## እስራኤላውያን በጭቆና ሥር

1 ቤተ ሰቦቻቸውን ይዘው ከያዕቆብ ጋር ወደ ግብፅ የሄዱት የእስራኤል ልጆች ስሞች እነዚህ ናቸው:- 2ሮቤል፣ ስምዖን፣ ሌዊ፣ ይሁዳ፣ 3ይሳኮር፣ ዛብሎን፣ ብንያምን 4ዳን፣ ንፍታሌም፣ ጋድና አሴር። 5የያዕቆብ ዘር ጠቅላላ ብዛት ሰባ[ሀ] ሲሆን፣ ዮሴፍ ግን ቀደም ብሎ በግብፅ ነበረ።

6ከጊዜ በኋላ ዮሴፍና ወንድሞቹ ያም ትውልድ በሙሉ ሞቱ፤ 7ይሁን እንጂ እስራኤላውያን እየተዋለዱ በዙ፤ ቍጥራቸው እጅግ ከመጨመሩም የተነሣ የግብፅን ምድር ሞሏት።

8በግብፅም፣ ስለ ዮሴፍ የማያውቅ አዲስ ንጉሥ ነገሠ። 9እርሱም ሕዝቡን እንዲህ አላቸው፤ "እነሆ፤ እስራኤላውያን በቍጥር በልጠውናል፤ ከእኛም ይልቅ እየበረቱ ነው፤ 10ቍጥራቸው እንዳይጨምር፣ ጦርነት ቢነሣ ከጠላቶቻችን ጋር አብረው እንዳይወጉንና ከምድሪቱም ኰብልለው እንዳይሄዱ ዘዴ እንፈልግ።"

11ስለዚህ እያስጨነቁ የግዳጅ ሥራ የሚያሠሯቸውን አሠሪ አለቆች ሾሙባቸው። እስራኤላውያንም ፊቶምና ራምሴ የተባሉ ንብረት ማከማቻ ከተሞችን ለፈርዖን ሠሩለት። 12ነገር ግን ባስጨነቋቸው መጠን የእስራኤላውያን ቍጥር በዛ፤ በምድሪቱም እየተስፋፉ ሄዱ፤ ከዚህም የተነሣ ግብፃውያኑ እስራኤላውያንን እጅግ ፈሯቸው፤ 13ጭካኔ በተሞላበት ሁኔታም ያሠሯቸው ጀመር። 14ጭቃ በማስቦካት፣ ጡብ በማሠራትና በእርሻም ሁሉ እያስጨነቁ ከባድ ሥራ እንዲሠሩ በማድረግ ሕይወታቸውን አስመረሩ፤ ግብፃውያኑ በሚያሠሯቸው ከባድ ሥራ ሁሉ ፈጽሞ አይራሩላቸውም ነበር።

15የግብፅም ንጉሥ ሲፓራና ፉሐ የተባሉትን ዕብራውያት ሴቶች አዋላጆች እንዲህ አላቸው፤ 16"የዕብራውያንን ሴቶች በማማጫው ድንጋይ ላይ በምታዋልዱበት ጊዜ የሚወለደው ሕፃን ወንድ ከሆነ ግደሉት፤ ሴት ከሆነች ግን በሕይወት ትኑር።" 17አዋላጆቹ ግን እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ስለፈሩ የግብፅ ንጉሥ ያዘዛቸውን አልፈጸሙም፤ ወንዶቹንም ልጆች በሕይወት እንዲኖሩ ተዉአቸው። 18ንጉሡም አዋላጆቹን ጠርቶ፣ "ለምንድን ነው ወንዶቹን ልጆች በሕይወት እንዲኖሩ የተዋችኋቸው? አላቸው።

19እነርሱም፣ "የዕብራውያን ሴቶች እንደ ግብፃውያን ሴቶች አይደሉም፤ ብርቱዎች ስለ ሆኑ አዋላጆች ከመድረሳቸው በፊት ይወልዳሉ" ሲሉ ለፈርዖን መለሱለት።

20ከዚህም የተነሣ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ለአዋላጆቹ መልካም ሆነላቸው፤ ሕዝቡም በቍጥር እየበዛና እያየለ ሄደ። 21አዋላጆቹም እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) በመፍራታቸው ቤተ ሰብ ሰጣቸው።

22ፈርዖንም፣ "የሚወለደውን ወንድ ልጅ[ለ]

1፥1 ዘፍ46፥8
1፥4 ዘፍ35፥22-26፤ዘኍ 1፥20-43
1፥5 ዘፍ46፥26
1፥6 ዘፍ50፥26፤ ሐሥ 7፥15
1፥7 ቍ9፤ ዘፍ12፥2፤ዘዳ7፥13፤ ሕዝ16፥7
1፥8 ኤር43፥11፤ 46፥2
1፥9 ቍ7፤ ዘፍ26፥16
1፥10 ዘፍ15፥13፤ ዘፀ3፥7፤18፥11፤ መዝ64፥2፤71፥10፤ 83፥3፤105፥24-25፤ ኢሳ53፥3፤ ሐሥ7፥17-19
1፥11 ዘፍ15፥13፤ 47፥11፤ዘፀ2፥11፤ 3፥7፤5፥4፡10፡13፡14፤ 6፥6-7፤ኢሱ9፥27፤ 1ነገ9፥21፤ 1ዜና22፥2፤ ኢሳ60፥10፤ 1ነገ9፥19፤2ዜና8፥4
1፥13 ቍ14፤ ዘፍ15፥13-14፤ ዘፀ5፥21፤16፥3፤ ዘሌ25፥43፡46፡53፤ ዘዳ4፥20፤26፥6፤ 1ነገ8፥51፤ መዝ129፥1፤ ኢሳ30፥6፤48፥10፤ ኤር11፥4
1፥14 ዘፍ11፥3፤ ዘፀ2፥23፤3፥9፤ ዘኍ20፥15፤ዘዳ26፥6 1ሳሙ10፥18፤ 2ነገ13፥4፤ዕዝ9፥9፤ ኢሳ14፥3፤ መዝ66፥11፤81፥6፤ ሐሥ7፥19
1፥15 ዘፍ35፥17
1፥16 ቍ22
1፥17 ቍ21፤1ሳሙ22፥17፤ምሳ16፥6፤ዳን3፥16-18፤ሐሥ4፥18-20 ፤5፥29
1፥19 ዘሌ19፥11፤ኢሱ2፥4-6፤1ሳሙ19፥14፤2ሳሙ17፥20
1፥20 ምሳ11፥18፤22፥8፤መክ8፥12፤ኢሳ3፥10፤ ዕብ6፥10
1፥21 ቍ17፤1ሳሙ2፥35፤2ሳሙ7፡11፡27-29፤1ነገ11፥38፤14፥10
1፥22 ቍ16፤ ዘፍ41፥1፤ሐሥ7፥19

[ሀ] 5 የማሶሬቱ ቅጅ (ዘፍ46፥27 ይመ)፣ የሙት ባሕር ጥቅልል እንዲሁም የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም (ሐሥ7፥14 እና የዘፍ 46፥7 ማብ ይመ)፣ *ሰባ አምስት* ይላሉ።

[ለ] 22 የማሶሬቱ ቅጅ፣ አሪተ ሳምራውያን፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም እንዲሁም ታርጕም *ከዕብራውያን የሚወለደውን* ይላሉ።

*1፥1-5፤* እነዚህ ቁጥሮች በግልጽ እንደሚያሳዩት ኦሪት ዘፀአት፣ የኦሪት ዘፍጥረት ተከታይ ነው። እስራኤላውያን በግብፅ ምድር 430 ዓመት ኖረዋል፤ (12፥4 ይመ)።

1፥1 *የእስራኤል ልጆች ስሞች እነዚህ ናቸው፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ አገላለጽ በዘፍ 46፥8 ላይ ይገኛል፤ በዚህ ክፍል ስማቸው የተዘረዘረው የያዕቆብ ልጆች ናቸው። *ከያዕቆብ ... የእስራኤል፤* ያዕቆብ ከዚህ በፊት እስራኤል የሚል ስም ተሰጥቶታል (ዘፍ 32፥28፤35፥10 እና ማብ ይመ)።

*1፥2-4፤* የልያና (ከሮቤል እስከ ዛብሎን) የራሔል ልጆች (ብንያም፤ በስም ዝርዝሩ ውስጥ የተጠቀሱ "ወደ ግብፅ የገቡት" ብቻ ናቸው። የዮሴፍ ስም አልተጠቀሰም)፤ ስም የተጠቀሰው በየዕድሜአቸው ቅደም ተከተል ስለሆነ፣ የልያና የራሔል አገልጋዮች ከወለዷቸው ወንዶች ልጆች በፊት ነው፤ የልያ አገልጋይ ዘለፋ ጋድንና አሴርን ስትወልድ የራሔል አገልጋይ ባላ ደግሞ ዳንንና ንፍታሌምን ወልዳለች፤ (ዘፍ 35፥23-26 ይመ)።

1፥5 *ሰባ፤* የዘፍ 46፥27 ማብ ይመ።

*1፥6-7፤* ዮሴፍ ከሞተበት ጊዜ አንስቶ በግብፅ አዲስ ንጉሥ (ቍ8) እስከተነሣበት ጊዜ ድረስ 200 ዓመት ይሆናል።

*1፥7፤* ሐሥ 7፥17 ይመ። እግዚአብሔር "ብዙ ተባዙ፤ ዘራችሁ ምድርን ይሙላ" የሚለውን ቃለ በረከት ለአዳም (ዘፍ 1፥28)፣ ለኖኅ (ዘፍ 8፥17፤ 9፥1፡7)፣ ለአብርሃም (ዘፍ 17፥2፡6፤ 22፥17)፣ ለይስሐቅና (ዘፍ 26፥4)፣ ለያዕቆብ (ዘፍ 28፥14፤ 35፥11፤ 48፥4) ሰጥቶአል። እስራኤል በግብፅ ምድር ለ430 ዓመት መጻተኛ ሆና በኖረችበት ዘመን እንኳ እግዚአብሔር ይህን ቃለ በረከት ፈጽሞአል። *የግብፅን ምድር ሞሏት፤* ይህን ሐረግ ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ ለአዳም የተሰጠውን ቃለ በረከት ያንፀባርቃል፤ (ዘፍ 1፥28)፤ እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሰጠው በረከት በእስራኤል ሕይወት ተፈጸመ። ከግብፅ የወጡት እስራኤላውያን ብዛት፣ "ሴቶችና ልጆች" ሳይቈጠሩ ስድስት መቶ ሺህ ወንዶች ነበሩ፤ (12፥37)። *ምድሪቱም፤* የጌሤምን ምድር ማለት ነው፤ (የዘፍ 45፥10 ማብ ይመ)።

*1፥8፤* የሐሥ 7፥18 ይመ። *አዲስ ንጉሥ፤* ምናልባት የ0ሥራ ስምንተኛው ሥርወ መንግሥት መሥራችና ሐይክሶስ የተባሉ ሕዝቦችን (ዝርያቸው ከሴም ወገን የሆኑና ግብፅን ይገዙ የነበሩ ሕዝቦች ናቸው)፤ ከግብፅ ያስወጣው አሙስ ተብሎ የሚጠራው ንጉሥ ሳይሆን አይቀርም።

1፥11 *አሠሪ አለቆች፤* ይህ ቃል የ18ኛው ሥርወ መንግሥት ፈርዖን በነበረው በቱትሞስ ሦስተኛው ዘመነ መንግሥት በቴብና መቃብር ግድግዳዎች ላይ ተጽፎ ይገኛል፤ (የመጽሐፉን መግቢያ ይመ)። *ራምሴ፤* የዘፍ 47፥11 ማብ ይመ። *ለፈርዖን፤* ቃሉ የተገኘው ከግብፃውያን ሲሆን፣ ትርጕሙም "ታላቅ ቤት" ማለት ነው፤ ቃሉ ግለሰቦች የሚጠሩበት ስም ሳይሆን የንግሥና ማዕረግ ነው።

1፥14 *ሕይወታቸውን አስመረሩ፤* የፋሲካን ምግብ "ከመራራ ቅጠል" (12፥8) ጋር ሲበሉ፣ በሕይወታቸው የሚያስታውሱት ትዝታ ነው። *በእርሻም ሥራ ሁሉ፤* ሌላው ሁሉ አልበቃ ብሎ ከዐባይ ወንዝ የመስኖ ውሃ ያስቀዷቸው ነበር (ዘዳ 11፥10 ይመ)።

1፥15 *ዕብራውያት፤* የዘፍ 14፥13ን ማብ ይመ። *ሲፓራና ፉሐ፤* ግብፃዊ ስም ሳይሆን ሴማዊ ስም ነው። እስራኤላውያን በቍጥር ብዙ ስለ ነበሩ፥ ምናልባት በሲፓራና በፉሐ ሥር ሌሎችም አዋላጆች ሳይኖሩ አይቀሩም።

1፥16 *በማማጫው ድንጋይ ላይ፤* የዕብራይስጡ ቃል በቁሙ ሲተረጐም "ሁለት ድንጋይ" ማለት ነው፤ አንድ ሴት ልጅ በምትወልድበት ጊዜ የምትቀመጠው በእነዚህ ድንጋዮች ላይ ነው።

*1፥17፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ነገር በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ስለመፈጸሙ የሐሥ 5፥29 ይመ። *እግዚአብሔርን*

ሁሉ ዐባይ ወንዝ ውስጥ ጣሉት፤ ሴት ልጅ ሁሉ ግን በሕይወት ትኑር" ሲል ሕዝቡን አዘዘ።

**የሙሴ መወለድ**

**2** በዚያን ጊዜ ከሌዊ ነገድ የሆነ አንድ ሰው አንዲት ሌዋዊት ሴት አገባ። [2]እርሷም ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች፤ ሕፃኑ መልከ መልካም መሆኑን ባየች ጊዜ ሦስት ወር ሸሸገችው። [3]ከዚያ በላይ ልትሸሽገው ባልቻለች ጊዜ ግን የደንገል ቅርጫት ወስዳ፣ በዝፍትና በቅጥራን ለቀለቀችው፤ ሕፃኑንም በውስጡ አስተኝታ ቅርጫቱን ዐባይ ወንዝ ዳር ቄጠማ መካከል አስቀመጠችው። [4]የሕፃኑም እኅት የሚደርስበትን ነገር ለማወቅ ራቅ ብላ ቆማ ታይ ነበር።

[5]በዚህ ጊዜ የፈርዖን ልጅ ልትታጠብ ወደ ዐባይ ወንዝ ወረደች፤ በምትታጠብበትም ጊዜ ደንገጥሮቿ በወንዙ ዳር ወዲያና ወዲህ ይሉ ነበር፤ በቄጠማውም መካከል የተቀመጠ ቅርጫት አይታ ከደንገጥሮቿ አንዷን እንድታመጣው ላከቻት። [6]ቅርጫቱን ስትከፍተው ሕፃኑን በውስጡ አየች፤ ያለቅስ ስለ ነበርም አዘነችለትና፣ "ከዕብራውያን ሕፃናት አንዱ መሆን አለበት" አለች።

[7]የሕፃኑ እኅት ለፈርዖን ልጅ፣ "ሕፃኑን እያጠባች የምታሳድግልሽ ከዕብራውያን ሴቶች መካከል ሞግዚት ላምጣልሽን? አለቻት።

[8]የፈርዖንም ልጅ፣ "መልካም፣ ሂጂ" አለቻት። ልጂቱም ሄዳ የሕፃኑን እናት ይዛ መጣች። [9]የፈርዖንም ልጅ ሴቲቱን፣ "ይህን ሕፃን ወስደሽ እያጠባሽ አሳድጊልኝ፤ ደመ ወዝ እከፍልሻለሁ" አለቻት። ሴትዮዋም ሕፃኑን ወስዳ አሳደገችው። [10]ሕፃኑም ባደገ ጊዜ ወደ ፈርዖን ልጅ አመጣችው፤ ልጇም ሆነ፤ እርሷም፣ "ከውሃ አውጥቼዋለሁና" ስትል ስሙን ሙሴ* ብላ ጠራችው።

**ሙሴ ወደ ምድያም ምድር ሸሸ**

[11]ሙሴ ካደገ በኋላ አንድ ቀን ወገኖቹ ወደሚገኙበት ስፍራ ወጣ፤ በዚያም ተገድደው ከባድ ሥራ ሲሠሩ ተመለከተ፤ ዕብራዊ ወገኑንም አንድ ግብፃዊ ሲደበድበው አየ። [12]ሙሴም አካባቢውን ቃኝቶ ማንም አለመኖሩን ካረጋገጠ በኋላ፣ ግብፃዊውን ገድሎ አሸዋ ውስጥ ደበቀው። [13]በማግሥቱም በወጣ ጊዜ ሁለት ዕብራውያን እርስ በርሳቸው ሲጣሉ አየ፤ ጥፋተኛውንም፣ "የገዛ ወገንህን የምትመታው ለምድን ነው?" አለው።

[14]ሰውየውም፣ "አንተን በእኛ ላይ ገዥና ዳኛ ማን አደረገህ? ግብፃዊውን እንደ ገደልኸው እኔንም ልትገድለኝ ትፈልጋለህን?" አለው። ሙሴም፣ "ለካስ ያደረግሁት ነገር ታውቆአል!" በማለት ፈራ።

[15]ፈርዖንም ይህን በሰማ ጊዜ፣ ሙሴን ሊገድለው ፈለገ፤ ሙሴ ግን ከፈርዖን ሸሽቶ ወደ ምድያም ሄደ፤ እዚያም እንደ ደረሰ በአንድ የውሃ ጉድጓድ አጠገብ ተቀመጠ። [16]የምድያም ካህን ሰባት ሴቶች ልጆች ነበሩት፤ እነርሱም ወደ ውሃው ጉድጓድ መጥተው የአባታቸውን በጎች ውሃ ለማጠጣት ገንዳውን ሞሉት። [17]እረኞችም መጥተው ሴቶቹን ሲያባርሯቸው ሙሴ ከተቀ

*10 በዕብራይስጥ ሙሴ የሚለው የቃል ድምፅ፣ *ማውጣት* ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ ድምፅ አለው።

2፥1 ቍ2፤ ዘፍ29፥34፤ዘፀ6፥20፤ ዘኍ26፥59
2፥2 ዘፍ39፥6፤ ዕብ11፥23
2፥3 ዘፍ6፥14፤ 41፥2፤ኢዮ8፥11፤ ኢሳ18፥2፤ሐሥ7፥21
2፥4 ዘፀ15፥20
2፥5 ዘፀ7፥15፤8፥20
2፥10 1ሳሙ1፥20፤ 2ሳሙ22፥17
2፥11 ዘፀ1፥11፤ ሐሥ7፥23፤ ዕብ11፥24-26፤
2፥13 ሐሥ7፥26
2፥14 ዘፍ13፥8፤ ሐሥ7፥27
2፥15 ዘፍ31፥21፤ ዘፀ4፥19፤ዕብ11፥27
2፥16 ዘፍ24፥11፤ 30፥38፤ዘፀ3፥1፤ 18፥1፤
2፥17 ዘፍ29፥10፤ 1ሳሙ30፥8፤ መዝ31፥2፤

*ስለ ፈሩ፤* የዘፍ 20፥11 ማብ ይመ።

2፥1 *አንድ ሰው ... አንዲት ሌዋዊት ሴት፤* እነዚህ ሰዎች ምናልባት ዓምራምና ዮኬቤድ ሊሆኑ ይችላል፤ (ሆኖም የ6፥20 ማብ ይመ)።

2፥2 *ሕፃኑ መልከ መልካም፤* ሙሴ "በእግዚአብሔር ፊት ያማረ ሕፃን" ነበር፤ (ሐሥ 7፥20፤ ዕብ 11፥23)። ይህ የሙሴን ከውሃው ውስጥ መውጣትና ከሞት መትረፍ የሚያወሳው ታሪክ፣ የኋላ ኋላ እግዚአብሔር በእርሱ አማካይነት ሕዝቡን በእርሱ ጥላ ሥር ከግብፅ ባርነት ነፃ እንደሚያወጣ የሚያመለክት ነው።

2፥3 *የደንገል ቅርጫት ወስዳ፤* ከዚህ ሐረግ በስተጀርባ ያሉት የዕብራይስጥ ቃላት የተገኙት ከግብፅ ቋንቋ ነው፤ "ቅርጫት" የሚለው ቃል ተጠቅሶ የምናገኘው እዚህ ላይ እና ስለ ኖኅ መርከብ በሚያወሳው ታሪክ ላይ ብቻ ነው፤ (የዘፍ6፥14 ማብ ይመ)። ከመጠኑ በአሻገር የሙሴ ቅርጫት በቅርጹ በኢሳያስ 18፥2 ላይ እንደ ተጠቀሰው ከደንገል የሚሠሩ ጀልባ ዎችን ይመስላል።

2፥4 *እኅቱም፤* ማርያም ናት፤ (15፥20 ይመ)።

2፥5 *የፈርዖን ልጅ፤* ምናልባት የ18ኛው ሥርወ መንግሥት ታላቋ ልዕልትና በኋላም ሐትሼፕሱት እየተባለች ትጠራ የነበረችው ንግሥት ናት። *ደንገጥሮቿም፤* በወንዙ ዳር ሆነው ልዕልቲቷን የሚያጥቡ አገልጋዮች ናቸው።

*2፥10፤* ሐሥ 7፥21-22 ይመ። በዚህ መጽሐፍ በመጀመሪያዎቹ ምዕራፎች ላይ እንደምንመለከተው፣ ፈርዖን እስራኤላውያንን ለማስጨነቅ ያደረገው ሙከራ የተጨናገፈው በሴቶች ነው፤ አዋላጆቹ (1፥17)፣ የዕብራውያን ሴቶች፣ (1፥19)፣ የሙሴ እናትና እኅት፣ (2፥3-4፡ 7-9) እንዲሁም የፈርዖን ሴት ልጅ፣ (2፥10) የፈርዖንን ክፉ አሳብ ከንቱ የሚያደርጉ፣ የእግዚአብሔር መሣሪያዎች ነበሩ። ይህም ፈርዖን የእግዚአብሔርን ሕዝብ ከገጸ ምድር ጠራርጎ ማጥፋት እንደማይችል ምፀታዊ በሆነ መንገድ ይገልጻል። *ሙሴ፤* ስሙ ከግብፃውያን የተወረሰ ሲሆን፣ ትርጕሙም "የተወለደ" ማለት ነው፤ ስሙ ለግብፅ ፈርዖኖች ከተሰጡት ማለትም እንደ አሙስ፣ (የ1፥8 ማብ ይመ)፣ ቱት ምስና ራምሴ፣ (የ1፥11 ማብ ይመ) ከሚባሉት ስሞች ጋር ይመሳሰላል። *ከውሃ ያወጣሁት፤* ይህ ሐረግና ሙሴ የሚለው ቃል በዕብራይስጥ ቋንቋ ተመሳሳይነት ያላቸው ሲሆኑ፣ ሙሴ ከናይል ወንዝ ታምራዊ በሆነ መንገድ መውጣቱን ያመለክታሉ። ለሙሴ የተሰጠው ስም እግዚአብሔር በእርሱ አማካይነት "በቀይ ባሕር" ላይ የፈጸመውን ታላቅ የማዳን ሥራ የሚያስታውስ ነው፤ (13፥17-14፡31 ይመ)።

2፥11-15፤ ሐ.ሥ 7፥23-29፤ ዕብ 11፥24-27 ይመ።

2፥11 *ሙሴ ካደገ በኋላ፤* አሁን ዕድሜው 40 ዓመት ነው፤ (ሐሥ 7፥23 ይመ)።

2፥14 *"ገዥና ዳኛ ማን አደረገህ?"* ይህን ቃል የተናገረው ሰው ሳያስተውለው ከ40 ዓመት በኋላ የሚፈጸም ትንቢት ተናገረ፤ (ሐ.ሥ 7፥27፡ 30፡35 ይመ)። *"ዳኛ"፤* የሚለውን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጥ ቃል በመጽሐፈ መሳፍንት እንደተጠቀሰው ሁሉ፤ "ታዳጊ" የሚል ትርጉም አለው (ሐሥ7፥35 ይመ)፤ ቃሉ በብሉይ ኪዳን እንዲሁም በጥንት ከነዓናውያን ሥነ ጽሑፍ ውስጥ "ገዥ" ከሚለው ጋር ተመሳሳይ ነው (ዘፍ 18፥25 እና ማብ ይመ)። *ሙሴም ... ፈራ፤* የዕብ 11፥27 ማብ ይመ።

2፥15 *ፈርዖንም፤* ምናልባት ቱትምስ ሦስተኛው ነው፤ (የመጽሐፉን መግቢያ ይመ)። *ወደ ምድያም፤* ምድያም ከሲና ተራራ በስተ ደቡብ ምሥራቅ፣ ከዐረብ አገር ደግሞ በስተ ምዕራብ እንዲሁም ከቀይ ባሕር (ከዐቃባ ባሕረ ሰላጤ) በስተምሥራቅ የሚገኝ ስፍራ ነው። ይህ ስፍራ ምድረ በዳና የፍርስራሽ ቀልል ሲሆን፣ ሙሴ ቀደም ሲል፣ በቤተ መንግሥት ይኖርበት ከነበረው ቤት በእጅጉ የሚለይ ነው። ሙሴ በምድያም ምድር 40 ዓመት ኖረ (ሐ.ሥ 7፥29-30 ይመ)።

2፥16 *የምድያም ካህን፤* ይህ ሰው ራጉኤል ሲሆን፤ (ቍ

መጠበት ተነሥቶ ተከላከለላቸው፤ በጎቻቸ ውንም አጠጣላቸው።

[18]ሴቶቹም ወደ አባታቸው ወደ ራጉ ኤል በተመለሱ ጊዜ፣ “ዛሬስ ያለወትሮ አችሁ እንዴት ፈጥናችሁ ተመለሳችሁ?” አላቸው።

[19]እነርሱም፣ “አንድ ግብፃዊ ከእረኞች እጅ አዳነን፤ እንዲያውም ውሃ ቀድቶ በጎ ቻችንን አጠጣልን” አሉት።

[20]አባታቸውም፣ “ሴቶች ልጆቹን የት አለ? ለምን ትታችሁት መጣችሁ? ጥሩትና አብሮን እንጀራ ይብላ” አላቸው።

[21]ሙሴም ከሰውየው ጋር ለመኖር ተስ ማማ፤ ራጉኤልም ልጁን ሲፓራን ዳረ ለት። [22]ሲፓራም ወንድ ልጅ ወለደች፤ ሙሴም፣ “በባዕድ አገር መጻተኛ ነኝ” ሲል የልጁን ስም ጌርሳም[ሙ] ብሎ ጠራው።

[23]ከብዙ ዓመት በኋላ፣ የግብፅ ንጉሥ ሞተ፤ እስራኤላውያንም በባርነት ከደረሰ ባቸው ግፍ የተነሣ ይጮኹ ነበር፤ ከባርነት ቀንበር ለመላቀቅ ያሰሙት ጩኸት ወደ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ደረሰ። [24]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) የጩኸታቸውን ሲቃ ሰማ፤ ከአብርሃም፣ ከይስሐቅና ከያዕቆብ ጋር የገባውንም ቃል ኪዳን አሰበ። [25]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) እስራኤላ ውያንን ተመለከተ፤ ስለ እነርሱም ገደደው።

## ሙሴና የሚንበለበለው ቍጥቋጦ

**3** አንድ ቀን ሙሴ የምድያም ካህን የሆነ ውን የአማቱን የዮቶር በጎችና ፍየሎች እየጠበቀ ሳለ፣ መንጋውን እየነዳ ወደ ምድረ በዳው ዳርቻ አምርቶ የእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ተራራ ተብሎ ወደሚጠራው ወደ ኮሬብ ቀረበ።

[2]እዚያም *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) መልአክ በቍጥቋጦው ውስጥ በሚንቀለቀል የእሳት ነበልባል መካከል ተገለጠለት። ሙሴም ቍጥ ቋጦው በእሳት ቢያያዝም እንኳ፣ አለመ ቃጠሉን አየ። [3]ሙሴም፣ “ቍጥቋጦው ለምን እንደማይቃጠል ቀረብ ብዬ ይህን አስገራሚ ነገር ልመልከት” አለ።

[4]ሙሴ ሁኔታውን ለመመልከት መቅረ ቡን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ባየ ጊዜ፣ ከቍጥ ቋጦው ውስጥ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) “ሙሴ፣ ሙሴ” ብሎ ጠራው፤ ሙሴም አቤት እነሆኝ አለው። [5]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም)፣ “ወደዚህ እንዳትቀ ርብ፤ ይህች የቆምኽባት ምድር የተቀደሰች ስለሆነች ጫማህን አውልቅ” አለው [6]ቀጥ ሎም፣ “እኔ የአባቶችህ የአብርሃም፣ የይ ስሐቅ፣ የያዕቆብ አምላክ (ኤሎሂም) ነኝ” አለው። በዚህ ጊዜ ሙሴ እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ፊት ለፊት ማየት ስለ ፈራ ፊቱን ሸፈነ።

[7]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ)፣ እንዲህ አለ “በግብፅ አገር የሚኖሩትን የሕዝቤን መከራ አይቻለሁ፤ ከአሠሪዎቻቸው ጭካኔ የተነሣ የሚያሰሙትንም ጩኸት ሰምቻ ለሁ፤ ሥቃያቸውንም ተረድቼአለሁ። [8]ስለ ዚህም ከግብፃውያን እ ጅ ልታደጋቸውና ማርና ወተት ወደምታፈሰው ሰፊና ለም ወደ ሆነችው ወደ ከነዓናውያን፣ ኬጢያ ውያን፣ አሞራውያን፣ ፌርዛውያን ኤዊያ ውያንና ኢያቡሳውያን ምድር ላወጣቸው ወርጃለሁ። [9]አሁንም የእስራኤል ልጆች ጩኸት ወደ እኔ ደርሷል፤ ግብፃውያን የሚ

2፥18 ዘፀ3፥1፤ 4፥18፤18፥1፡5፡12፤ ዘኍ10፥29
2፥20 ዘፍ18፥2-5
2፥21 ዘፀ4፥25፤ 18፥2፤ዘኍ12፥1
2፥22 ዘፍ23፥4፤ መሳ18፥30፤ ዕብ11፥13
2፥23 ቍ24፤ ዘፀ4፥19፤1፥14፤ ዘፀ 3፥7፡9፤6፥5፤ ዘኍ20፥15-16፤ ዘዳ26፥7፤ መሳ2፥18፤1ሳሙ12፥8፤መዝ5፥2፤18፥6፤ 39፥12፤81፥7፤102፥1 ሐሥ7፥30፤ያዕ5፥4
2፥24 ዘፍ8፥1፤ 9፥15፤ 15፥15፤ 17፥4፤22፥16-18፤ 26፥3፤28፥13-15፤ ዘፀ32፥13፤ 2ነገ 13፥23፤ መዝ105፥10:42፤ ኤር14፥21
2፥25 ዘፀ3፥7፤ 4፥31፤ሉቃ1፥25
3፥1 ቍ12፤ ዘፀ2፥18፡16፤4፥27፤ 17፥6፤18፥5፤19፥1-11፤24፥13፤33፥6፤ ዘዳ1፥2፡6፤4፥10፡11፡ 15፤5፥2፤29፥1፤ መሳ1፥16፤1ነገ19፥8፤ ሚል4፥4፤
3፥2 ቍ4፤ ዘፍ16፥7፤ዘፀ12፥23፤ 19፥18፤2፥2-6፤ዘዳ 33፥16፤1ነገ19፥12፤ ማር12፥26፤ሉቃ20፥37፤ሐሥ5፥19፤7፥30
3፥4 ዘፍ31፥11፤ዘፀ 4፥5፤19፥3፤ዘሌ1፥1፤ 1ሳሙ3፥4፤ኢሳ6፥8
3፥5 ዘፍ28፥17፤ ኤር30፥21፤ ሐሥ 7፥33
3፥6 ዘፍ24፥12፤ዘፀ 4፥5፤24፥11፤33፥20፤ መሳ13፥22፤1ነገ 19፥13፤ ኢዮ13፥11፤ 23፥16፤30፥15፤ኢሳ6፥5፤ ማቴ22፥32፤ማር12፥26፤ሉቃ20፥37፤ሐሥ3፥13፤7፥32፤
3፥7 ቍ16፤ዘፍ16፥11፤ዘፀ፥10፤2፥25፤1ሳሙ1፥11፤9፥16፤ነህ9፥9፤ መዝ106፥44 ሐሥ7፥34 3፥8 ቍ17፤ዘፍ11፥5፤12፥7፤15፥14፤ 18-21፤ዘፀ13፥5፤33፥3፤ዘሌ20፥24፤ዘኍ13፥27፤ዘዳ1፥25፤6፥3፤8፥7-9፤ 11፥9፤26፥9፤27፥3፤ኢሱ5፥6፤11፥3፤መሳ3፥3፤2ሳሙ24፥7፤ዕዝ9፥1፤ ኤር11፥5፤32፥22፤ሕዝ20፥6፤ሐሥ7፥34 3፥9 ዘፀ1፥14፤ዘኍ10፥9

[ሙ]22 በዕብራይስጥ ጌርሳም የሚለው ቃል ድምፅ፣ *መጻተኛ በዚያ አለ* ከሚለው ሐረግ ጋር ተመሳሳይ ድምፅ አለው።

18 ይመ)፣ የስሙ ትርጒም “የእግዚአብሔር ወዳጅ” ማለት ነው። ሌላው ስሙ ዮቶር ሲሆን፣ (3፥1 ይመ) ትርጒሙም “የተ ከበርኸው” ማለት ነው።

2፥23 *ከብዙ ዓመት በኋላ፤* ቱትምስ ሦስተኛው (የቍ 15 ማብ ይመ) ረጅም ዓመት ኖሮአል።

2፥24 *ከአብርሃም ... ጋር የገባውን ቃል ኪዳን፤* ዘፍ 15፥17-18፤ 17፥7 እና ማብ ይመ። *ከይስሐቅና፤* ዘፍ 17፥19፤ 26፥24 ይመ። *ከያዕቆብ፤* ዘፍ 35፥11-12 ይመ።

*3፥1፤* እንደ ዳዊት ሁሉ፣ (2ሳሙ 7፥8) ሙሴም የእግዚአ ብሔርን ሕዝብ እንዲጠብቅ የተጠራው ከእረኝነት ነው። *ዮቶር፤* የ2፥16 ማብ ይመ። *ኮሬብ፤* የስሙ ትርጒም “ምድረ በዳ” ወይም “የፍርስራሽ ቀልል” ማለት ነው፤ ይህ ስም (1) የሲና ተራራ የሚለው ሌላው ስሙ ነው፤ ኤልያም (2) በዚሁ አካባቢ ከሲና ባሕር ስርና በስተደቡብ ምሥራቅ የሚገኝ ሌላ ትልቅ ተራራ ነው። በዘልማድ እንደሚነረገው ከሆነ የኬብሮን ተራራ ተብሎ የሚጠራው፣ 1980.33 ሜትር ርዝመት ያለው የራስ ኤስ ሳፍሳፍ ሲሆን፣ የሲና ተራራ ተብሎ የሚጠራው ደግሞ፣ 2254.53 ሜትር ርዝመት ያለው የዮቤል ሙሳ (“የሙሴ ተራራ”) ነው፤ ሆኖም ነገሩ እርግጥ ስለመሆኑ በውል የሚታወቅ ነገር የለም።

3፥2 *የእግዚአብሔር መልአክ፤* በቍጥር 4 ላይ “እግዚአ ብሔር (ያህዌ)” እና “እግዚአብሔር (ኤሎሂም)” ተብሎአል (የዘፍ 16፥7 ማብ ይመ)። *በሚንቀለቀል የእሳት ነበልባል ... ተገለጠለት፤* እግዚ አብሔር ራሱንም ሆነ ፈቃዱን ሲገልጥ አብዛኛውን ጊዜ በእሳት ነበ ልባል ታጅቦ ነው፤ (13፥21፤ 19፥18፤ 1ነገ 18፥24፡38 ይመ)።

*3፥4፤* እውነተኞች ነቢያት ሁሉ የተጠሩት በእግዚአብሔር ነው፤ (ለምሳሌ 1ሳሙ3፥4፤ ኢሳ6፥8፤ ኤር1፥4-5፤ ሕዝ2፥1-8፤ሆሴ1፥2፤ አሞ 7፥15፤ ዮና 1፥1-2 ይመ፤ እንዲሁም የ7፥1-2 ማብ ይመ)። *ሙሴ! ሙሴ! ... እነሆ አለሁ!* የዘፍ22፥1፡11 ማብ ይመ።

3፥5 *ጫማህን አውልቅ፤* አንዳንዶች ወደ ቅዱስ ቦታ ሲገቡ የሚፈጽሙት ሥርዐት ነው። *የተቀደሰች፤* ምድሪቱ በተፈጥሮዋ ቅድስት አይደለችም፤ ሆኖም እግዚአብሔር ስለተገ ለጠባት የተ ቀደሰች ሆናለች (ዘፍ 2፥3 ይመ)። መቀደስ ለእግዚአብሔር አገልግሎት ሙሉ በሙሉ መስጠትንና ከተራው ስፍራ መለየትን ያካትታል።

*3፥6፤* 2፥24 እና ማብ ይመ። *እግዚአብሔርን ፊት ለፊት ማየት ስለፈራ፤* የዘፍ 16፥13፤ 32፥30 ማብ ይመ። የኋላ ኋላ ሙሴ የእግዚአብሔር አገልጋይ ለመሆን በመታደሉ በሲና ተራራ ላይ ከእግዚአብሔር ጋር ተነጋገረ፤ (19፥3)፣ የእግዚአብሔርንም ክብር ለማየት ጥያቄ አቀረበ፤ (33፥18)።

*3፥8፤ ልታደጋቸውና ... ወርጃለሁ፤* እግዚአብሔር ለመፍ ረድም ሊመጣ ይችላል፤ (ዘፍ 11፥5-9፤ 18፥21 ይመ)። *ማርና ወተት ወደምታፈሰው ... ምድር፤* ለተራራማው ለከነዓን ምድር የተሰጠ ስም ነው፤ ይህ ስፍራ በመጀመሪያ የግጦሽ ስፍራ ነበር፤ (የኢሳ 7፥15 ማብ ይመ)። *ከከነዓናውያን ... ኢያቡሳውያን፤* የዘፍ 10፥6፡15-16፤ 13፥7 ማብ ይመ። በከነዓን የሚገኙ ሕዝቦች ቍጥር ከሁለት፤ (ዘፍ 13፥7 ይመ) እስከ አምስት (ዘኍ 13፥29 ይመ) ከዚያም እስከ ስድስት (እዚያ ላይ እንደተጠቀሰው፤ እንዲሁም ዘዳ 7፥11 ይመ) እስከ ዐሥር (ዘፍ 15፥19-21 ይመ) እስከ ዐሥራ ሁለት (ዘፍ10፥15-18 ይመ) ይደርሳሉ። አብዛኛውን ጊዜ ግን የሰባቱ ስም ብቻ ነው የተጠቀሰው፤ (ዘዳ 7፥1 ይመ)፤ ይህም የሆነው ሰባት እንደ ፍጹም ቍጥር ስለሚታይ ነው (የዘፍ 4፥17-18 ማብ ይመ)።

ያደርሱባቸውን ግፍ አይቻለሁ። [10]በል እን ግዲህ ና፤ ሕዝቤን፣ የእስራኤልን ልጆች ከግብፅ ምድር እንድታወጣቸው ወደ ፈር ዖን እልክሃለሁ"።

[11]ሙሴ እግዚአብሔርን (ኤሎሂም)፣ "ወደ ፈር ዖን የምሄድና የእስራኤልን ልጆች ከግብፅ የማወጣ እኔ ማን ነኝ? አለው።

[12]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም)፣ "እኔ ከአንተ ጋር እሆናለሁ፤ እኔ የላክሁህ ለመሆኑ ምልክቱ ይህ ነው፤ ሕዝቡን ከግብፅ ካወጣሃቸው በኋላ በዚህ ተራራ ላይ እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ታመልካላችሁ" አለው።

[13]ሙሴም እግዚአብሔርን (ኤሎሂም)፣ "ወደ እስ ራኤል ልጆች ሄጄ፣ 'የአባቶቻችሁ አም ላክ ወደ እናንተ ልኮኛል' ስላቸው 'ስሙ ማን ነው?' ብለው ቢጠይቁኝ ምን እላቸዋ ለሁ?" አለው።

[14]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) ሙሴን፣ "እኔ፣ ያለሁና የምኖር ነኝ[ሠ] (ያህዌ)፤ ስለዚህም፣ 'ያለና የሚኖር' ልኮኛል ብለህ ንገራቸው" አለው።

[15]ደግሞም እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ሙሴን፣ "የአባቶቻችሁ የአብርሃም አምላክ፣ የይስሐቅ አምላክ፣ የያዕቆብ አምላክ የሆነው *እግዚ አብሔር*[ረ] (ያህዌ) ወደ እናንተ ልኮኛል፤ ስሜም ለዘለዓለም ይኸው ነው፤ ወደፊት በተከታ ታይ በሚነሣው ትውልድ ሁሉ የምታስበው በዚህ ስም ነው ብለህ ለእስራኤል ልጆች ንገራቸው" አለው።

[16]"ሂድና የእስራኤልን አለቆች ሰብስ በህ፣ የአባቶቻችሁ የአብርሃም፣ የይስሐቅና የያዕቆብ አምላክ የሆነው *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ተገለጠልኝና እንዲህ አለኝ፤ ጐብኝቻች ኋለሁ፤ በግብፅ የደረሰባችሁንም አይቻ ለሁ። [17]ስለዚህም በግብፅ ከምትቀበሉት መከራ አውጥቼ ማርና ወተት ወደምታ ፈስው ወደ ከነዓናውያን፣ ወደ ኬጢያው ያን፣ ወደ አሞራውያን፣ ወደ ፌርዛውያን፣ ወደ ኤዊያውያንና ኢያቡሳውያን ምድር አገ ባችኋለሁ ብሎአል ብለህ ንገራቸው" አለኝ።

[18]"የእስራኤል አለቆችም ይሰሙሃል። አንተና የእስራኤል አለቆች ወደ ግብፅ ንጉሥ ትሄዱና፣ 'የዕብራውያን አምላክ *እግ ዚአብሔር* (ያህዌ) ተገለጠልን፤ ስለዚህም ወደ ምድረ በዳ የሦስት ቀን መንገድ ተጕዘን ለአምላካችን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) መሥዋዕት እንድናቀርብ ፍቀድልን' ብላችሁ ትነግሩ ታላችሁ። [19]የግብፅ ንጉሥ ግን በኀያል ክንድ ካልተገደደ በስተቀር መቼም እንደ ማይለቃችሁ አውቃለሁ። [20]ስለዚህ እኔ እጅግ ድንቅ የሆኑ ታምራትን እዚያው እመ ካከላቸው በማድረግ ክንዴን ዘርግቼ ግብፃ ውያንን እመታቸዋለሁ፤ ከዚያም በኋላ እን ድትሄዱ ይለቃችኋል።

[21]ይህ ሕዝብ በግብፃውያን ዘንድ የመ ወደድን ጸጋ እንዲያገኝ ስለማደርግ በምት ወጡበት ጊዜ ባዶ እጃችሁን አትሄዱም። [22]እያንዳንዷ ዕብራዊት ከጎረቤቷም ይሁን አብራት ከምትኖረው ግብፃዊት የብርና

3፥10 ዘፀ4፥12፤ 6፥13:26፤12፥41:51 20፥2፤ዘዳ4፥20፤ ኢሱ24፥5፤1ሳሙ12፥ 6:8፤መዝ105፥26፤ 1ነገ8፥16፤ሚክ6፥4፤ ሐሥ7፥34 3፥11 ዘፀ4፥10፤ 6፥12:30፤መሳ6፥15፤ 1ሳሙ9፥21፤15፥17፤ 18፥18፤2ሳሙ7፥18፤ 2ዜና2፥6፤ኢሳ6፥5፤ ኤር1፥6 3፥12 ቍ1፤ዘፍ 26፥3፤ዘፀ14፥22፤ዘኍ 26፥10፤ኢሱ2፥12፤ መሳ6፥17፤መዝ86፥ 17፤ኢሳ7፥14፤8፥18፤ 20፥3፤ኤር44፥29፤ ሐሥ7፥7፤ሮሜ8፥31፤ 3፥13 ዘፍ32፥29 3፥14 ዘፀ6፥2-3፤ ዮሐ8፥58፤ዕብ13፥8፤ ራእ1፥8፤4፥8 3፥15 ዘፍ24፥12፤ 31፥42፤ዘፀ6፥3:7፤ 15፥3፤23፥21፤ 34፥5-7፤ዘሌ24፥11፤ ዘዳ28፥58፤መዝ30፥ 4፤83፥18፤96፥2፤97፥ 12፤135፥13፤145፥21 ኢሳ42፥8፤ኤር16፥21 ፤33፥2፤ሆሴ12፥5፤ መዝ45፥17፤72፥17፤ 102፥12፤ዳን2፥23፤ 102፥12፤ዳን2፥23፤ 3፥16 ዘፍ24፥12፤ ዘፀ4፥29:31፤17፥5፤ ዘሌ4፥15፤ዘኍ11፥16 ፤16፥25፤ዘዳ5፥23፤ 19፥12፤መሳ8፥14፤ ሩት4፥2፤2ነገ19፥16 ፤2ዜና6፥20፤መዝ 33፥18፤66፥7፤ምሳ 31፥23፤ሕዝ8፥11፤ 3፥17 ቍ8፤ዘፍ 15፥16፤46፥4፤ዘፀ6፥6 3፥18 ዘፍ14፥13፤ 30፥36፤ዘፀ4፥1:8:23: 31፤5፥1:3፤6፥11:12: 30፤7፥16፤8፥20:27፤9፥13፤10፥9:26፤ዘኍ23፥4:16 3፥19 ዘፀ4፥21 ፤6፥6፤7፥3፤10፥1፤11፥9፤ዘዳ4፥34፤2ዜና6፥32 3፥20 ዘፀ4፥21፤6፥1: 6፤7፥3:4-5፤9፥15፤11፥1:9:10፤12፥31-33፤13፥3:9:14:16፤15፥6:12 ፤34፥10፤ዘኍ14፥11፤ዘዳ3፥24፤4፥34:37፤5፥15፤6፥22፤7፥8፤26፥8፤ 2ነገ17፥36፤2ዜና6፥32፤ነህ9፥10፤መዝ71፥9፤72፥18፤77፥14፤78፥43፤ 86፥10፤105፥27፤106፥22፤118፥15-16፤135፥9፤136፥4:12፤ኢሳ 41፥10፤63፥12፤ኤር21፥5፤32፥20፤51፥25፤ዳን9፥15፤ሚክ7፥15፤ሐሥ 7፥36 3፥21 ዘፍ39፥21፤ዘፀ11፥2፤2ዜና30፥9፤ነህ1፥11፤መዝ 105፥37፤106፥46፤ኤር42፥12

[ሠ]14 ወይም እኔ የምሆነው እኔኑ ነው ማለት ሊሆን ይችላል።
[ረ]15 በዕብራይስጥ እግዚአብሔር የሚለው ቃል ድምፅ በቍ 14 ላይ፣ እኔ ነኝ ከሚለው ሐረግ ጋር ተመሳሳይ ድምፅ አለው። ያህዌ የሚለውም የቃል ውልደት እኔ ነኝ ከሚለው ሐረግ ነው።

3፥10 *ፈርዖን፤* ምናልባት አሙንሖቴፕ ሁለተኛው ሳይሆን አይቀርም (የመጽሐፉን መግቢያ ይመ)።

*3፥11* ሙሴ ፈቃደኛ አለመሆኑን ለመጀመሪያ ጊዜ ገለጸ፤ (ቍ 13፤4፥1:10:13 ይመ)።

3፥12 *እኔ ከአንተ ጋር እሆናለሁ፤* የዘፍ 26፥3 ማብ ይመ። እዚህ ላይ "እኔ ... እሆናለሁ" ተብሎ ከዕብራይስጡ የተ ተረጐመው ሐረግ በቍጥር 14 ላይ "እኔ ... ነኝ" ተብሎ ከተተ ረጐመው ጋር አንድ ነው። *ምልክት፤* እግዚአብሔር የተናገረውን ነገር በእርግጥ እንደሚፈጽም የሚያረጋግጥ ተጨባጭ ማስረጃ ነው፤ (የ4፥8፤ የዘፍ 15፥8 ማብ ይመ)።

3፥13፤ ሙሴ ፈቃደኛ አለመሆኑን ለሁለተኛ ጊዜ ገለጸ። *ስሙ ማን ነው?* እግዚአብሔር ስሙን ለሙሴ ገና አልገለጠ ለትም ነበር፤ (ቍ 6 ይመ፤ ከዘፍ 17፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥14 *እኔ ያለሁና የምኖር ነኝ፤* እግዚአብሔር በእስራኤል መካከል መታወቅና መመለክ የሚፈልገው በዚህ ስም ነው፤ ይህ ስም እግዚአብሔር በባሕርዩ ታማኝ አምላክ መሆኑን የሚገልጽና ከሕዝቡም ፍጹም አምልኮን የሚፈልግ፣ መሆኑን የሚያሳይ ነው፤ (በቍ 12 ላይ "እሆናለሁ" የሚለው ቃል "ከአንተ ጋር" ከሚለው ሐረግ ጋር እንደተሳሰረ ይመ፤ እንዲሁም 34፥5-7 ይመ)። *እኔ ... ነኝ፤* ይህ ስም በአጭሩ ሲጻፍ ምን እንደሚ መስል በመዝሙር 50፥21 ላይ ተጠቅሶአል። ኢየሱስ በዚህ ስም ራሱን በመጥራት አምላክ መሆኑን አረጋግጦአል፤ አይሁድ ሊወ ግሩት የነበረውም ይህንን ስም በመጠቀሙ ነው፤ (ዮሐ 8፥58-59 ይመ)።

3፥15 *እግዚአብሔር፤* በዕብራይስጡ ቅጅ ላይ ያህዌ ይላል፤ (የዘዳ 28፥58 ማብ ይመ)። ትርጕሙም "ያለ" ወይም "የሚኖር" ማለት ነው።

3፥16 *አለቆች፤* ይህንን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራ ይስጡ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም "ጢማሞች" ማለት ሲሆን፣ ይህም አንድ ሰው በሽምግልና ጊዜው ለማገልገል የሚያስፈ ልገውን ዕድሜ፣ ጥበብና ልምድ ሊኖረው እንደሚገባ ያሳያል። "ሽማግሌዎች" የቤተ ሰብና የነገድ ራስ በመሆናቸው በባቢ ሎናውያን፣ በሒታውያን፣ በግብፃውያን (ዘፍ 50፥7 ይመ)፣ በሞዓባውያንና በምድያማውያን (ዘኍ 22፥7 ይመ) ዘንድ ሕዝብ የሚያውቀው ሥልጣን አላቸው። ሥራቸውም የፍርድ ውሳኔዎ ችን ማስተላለፍ ነው፤ (ዘዳ 22፥13-19 ይመ)፣ ይኸውም ወታደራዊ አመራርና (ኢሱ 8፥10) ምክር መስጠት ነው፤ (1ሳሙ 4፥3 ይመ)።

3፥18 *የዕብራውያን፤* የዘፍ 14፥13 ማብ ይመ። *የሦስት ቀን መንገድ፤* ጕዞው ልክ ሦስት ቀን ይወስዳል ለማለት ሳይሆን፣ ምናልባት አጭር ጕዞ መሆኑን ለመግለጽ የሚያገለግል አባባል ሳይሆን አይቀርም። *ምድረ በዳ፤* እግዚአብሔር ከሙሴ ጋር የተገናኘው በዚህ ስፍራ ነው፤ (ቍ 1-2 ይመ)፤ እንደገና የሚገናኘውም በዚሁ ስፍራ ነው፤ (ቍ 12 ይመ)።

3፥20 *ታምራት፤* እግዚአብሔር በግብጻውያን ላይ የሚያመጣውን መቅሠፍት የሚያመለክት ትንቢት ነው፤ (7፥14-12፥30 ይመ)።

*3፥21-22፤* 11፥2-3፤ 12፥35-36 ይመ።

3፥21 *በምትወጡበት ጊዜ ባዶ እጃችሁን አትሄዱም፤* እስ ራኤላውያን ለ400 ዓመት ካገለገሉ በኋላ፣ "ብዙ ሀብት ይዘው እንደሚመለሱ" እግዚአብሔር ለአብርሃም ቃል ገብቶለት ነበር፣ (ዘፍ 15፥14፤ መዝ 105፥37 ይመ)። እስራኤል ራሷ ነጻ ለሚወጡ ባሪያዎች ስጦታን በመስጠት በዚህ መርሕ መሠረት መኖር ይጠ

የወርቅ ጌጣጌጦች እንደዚሁም ልብስ እንድ ትሰጣት ትጠይቅ። እነዚህንም ሁሉ ወስዳችሁ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻችሁን ታስጌጧቸዋላችሁ፤ ታለብሷቸዋላችሁም። በዚህም መንገድ የግብፃውያኑን ሀብት በእጃችሁ አግብታችሁ ትወጣላችሁ።"

## ለሙሴ የተሰጡ ምልክቶች

**4** ሙሴም "ባያምኑኝስ፤ ቃሌን ባይቀበሉስ፤ 'እግዚአብሔር (ያህዌ) አልተገለጠልህም' ቢሉኝስ?" ብሎ መለሰ። 2እግዚአብሔርም (ያህዌ)፣ "በእጅህ የያዝሀት እርሷ ምንድን ናት?" ሲል ጠየቀው፤ እርሱም መልሶ፣ "በትር ናት" አለው።

3እግዚአብሔርም (ያህዌ)፣ "መሬት ላይ ጣላት" አለው።

ሙሴ በትሩን መሬት ላይ ጣላት፤ እባብም ሆነች፤ ከአጠገቧም ሸሸ። 4እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "በል እጅህን ዘርጋና ጅራቷን ያዛት" አለው። ሙሴም እጁን ዘርጎቶ ሲይዛት እባቧ ተለውጣ በእጁ ላይ እንደ ገና በትር ሆነች። 5እግዚአብሔርም (ያህዌ) "ይህ የሆነው የአባቶቻቸው አምላክ፣ የአብርሃም አምላክ፣ የይስሐቅ አምላክ፣ የያዕቆብ አምላክ እግዚአብሔር (ያህዌ) የተገለጠልህ መሆኑን እንዲያምኑ ነው" አለው።

6እግዚአብሔርም (ያህዌ) ደግሞ፣ "እጅህን ብብትህ ውስጥ አስገባ" አለው። ሙሴም እጁን ብብቱ ውስጥ አስገባ፤ ከብብቱ ውስጥ ባወጣት ጊዜ እጁ እንደ በረዶ ለምጽ^ ሆነች።

7"አሁንም ደግሞ እጅህን ወደ ብብትህ መልሰህ አስገባ" አለው። ሙሴም እጁን መልሶ ብብቱ ውስጥ አስገባ፤ እንደገና እጁን ከብብቱ ውስጥ ባወጣት ጊዜ፣ ተመልሳ እንደ ሌላው የሰውነቱ ክፍል ሆነች።

8እግዚአብሔርም (ያህዌ)፣ "እንግዲህ ባያምኑህ ወይም የመጀመሪያውን ታምራዊ ምልክት ባይቀበሉ እንኳ ሁለተኛውን ያምናሉ። 9እነዚህን ሁለት ምልክቶች ባያምኑ ወይም ቃልህን ባይቀበሉ ግን፣ ከዐባይ ወንዝ ጥቂት ውሃ ቀድተህ በደረቅ ምድር ላይ አፍስሰው። ከወንዙም ቀድተህ ያፈሰስኸው ውሃ በምድር ላይ ደም ይሆናል።"

10ሙሴም እግዚአብሔርን ጌታ ሆይ (ያህዌ አዶናይ)፣ ቀድሞም ሆነ፣ አንተ ከባሪያህ ጋር ከተነጋገርህ ወዲህ፣ ከቶ አንደበተ ርቱዕ ሰው አይደለሁም። እኔ ኰልታፋና ንግግር የማልችል ሰው ነኝ" አለው።

11እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን፣ "ለሰው አንደበቱን የሰጠው ማነው? ሰውን ደንቆሮ ወይም ዲዳ የሚያደርገው ማነው? ዐይን የሚሰጥ ወይም ዕውር የሚያደርገውስ ማነው? እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) አይደለሁምን?"

12በል አሁን ሂድ፤ እኔ እንድትናገር አደርግሃለሁ፤ የምትናገረውንም አስተምርሃለሁ" አለው። 13ሙሴ ግን፣ "ጌታ ሆይ (አዶናይ)፤ እባክህ ሌላ ሰው ላክ" አለው።

14በዚህ ጊዜ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ቍጣ በሙሴ ላይ ነደደ፣ "ሌዋዊው ወንድምህ አሮን አለ አይደል? እርሱ ጥሩ እንደሚናገር ዐውቃለሁ፤ እንዲያውም አሁን ወደ አንተ እየመጣ ነው፤ በሚያይህም ጊዜ ከልቡ ደስ ይለዋል። 15ለእርሱ ትነግረዋለህ፤ የሚናገራቸውንም ቃላት በአንደበቱ ታኖራለህ፤ ሁለታችሁም በትክክል እንድትናገሩ እረዳችኋለሁ፤ ምን ማድረግ እንዳለባችሁም አስተምራችኋለሁ። 16አንተ እንደ አምላኩ ሆነህ ትነግረዋለህ፤ እርሱም እንደ አንደበትህ ሆኖ ለሕዝቡ ይናገርልሃል። 17ታምራዊ ምልክት እንድታሳይባት ይህችን በትር በእጅህ ይዘህ ሂድ።"

## ሙሴ ወደ ግብፅ ተመለሰ

18ሙሴም ወደ አማቱ ወደ ዮቶር ተመልሶ ሄደና፣ "ወገኖቼ እስካሁን በሕይወት መኖራቸውን አይ ዘንድ ወደ ግብፅ ተመልሼ እንድሄድ እባክህ ፍቀድልኝ" አለው።

ዮቶርም፣ "ሂድ፤ በሰላም ያግባህ" አለው።

19ሙሴ በምድያም ሳለ እግዚአብሔር (ያህዌ)፣ "አንተን ሊገድሉህ የሚፈልጉ ሰዎች ሁሉ ሞተዋልና ተመልሰህ ወደ ግብፅ ሂድ" አለው። 20ስለዚህ ሙሴ ሚስቱንና ልጆቹን በአህያ ላይ አስቀምጦ፣ ወደ ግብፅ አገር

3፥22 ዘፍ 15፥14፤ ዘፀ11፥2፤12፥35፤ ዕዝ1፥4፡6፤7፥16፤ ኢዮ27፥16-17፤ መዝ105፥37፤ ሕዝ39፥10፤29፥10
4፥1 ዘፀ3፥18
4፥2 ቍ 17:20፤ ዘፍ38፥18፤ዘፀ7፥19፤8፥5:16፤14፥16:21፤17፥5-6:9፤ዘኍ17፥2፤20፥8፤ኢሱ8፥18፤ መሳ6፥21፤1ሳሙ14፥27፤2ነገ4፥29
4፥3 ዘፀ7፥8-12:15
4፥5 ቍ 31፤ዘፀ3፥6፤14፥31፤19፥9
4፥6 ዘሌ13፥2:11፤ ዘኍ12፥10፤ዘዳ24፥9፤ 2ነገ5፥1:27፤2ዜና 26፥21
4፥7 2ነገ5፥14፤ ማቴ8፥3፤ሉቃ17፥12-14
4፥8 ቍ 30፤ዘፀ 3፥18፤መሳ6፥17፤1ነገ 13፥3፤ኢሳ7፥14፤ኤር 44፥29
4፥9 ዘፀ7፥17-21
4፥10 ዘፀ3፥11
4፥11 መዝ94፥9፤ 146፥8፤ማቴ11፥5፤ ሉቃ1፥20:64፤ ዮሐ10፥21
4፥12 ቍ 15-16፤ ዘፀ3፥10፤ዘኍ23፥5፤ ዘዳ18፥15:18፤ኢሳ 50፥4፤51፥16፤ኤር 1፥9፤ማቴ10፥19-20፤ ማር13፥11፤ሉቃ 12፥12
4፥13 ዮና1፥1-3
4፥14 ቍ 27፤ዘኍ 11፥1:10:33፤12፥9፤ 16፥15፤22፥22፤ 24፥10፤32፥13፤ዘዳ 7፥25፤ኢሱ7፥1፤ኢዮ 17፥8፤1ሳሙ10፥2-5
4፥15 ቍ 30፤ ዘኍ23፥5:12:16፤ ዘዳ18፥18፤ኢሱ1፥8፤ ኢሳ51፥16፤59፥21፤ ኤር1፥9፤31፥33
4፥16 ዘፀ7፥1-2፤ዘኍ33፥1፤ኤር15፥19፤36፥6፤መዝ77፥20፤105፥26፤ሚክ6፥4
4፥17 ቍ 2:20፤ ዘፀ17፥9፤17፥9-21፤ 8፥5:16፤9፥22፤ 10፥12-15:21-23፤ 14፥15-18:26፤ ዘኍ14፥11፤ዘዳ4፥34 መዝ74፥9፤78፥43፤105፥27
4፥19 ዘፀ2፥15:23፤ማቴ2፥20 4፥20 ቍ 2፤ዘፀ2፥22፤18፥3፤ ሐሥ7፥29

^6 በዕብራይስጥ፣ ለምጽ የሚባለው ቆዳን ለሚያጠቁ በሽታዎች ሁሉ የሚውል እንጂ ቁምጥናን ወይም ለምጽን የሚያሳይ አይደለም።

በቅባት ነበር፤ (ዘዳ 15፥12-15 ይመ)።

*4፥11* ሙሴ ፈቃደኛ አለመሆኑን ለሦስተኛ ጊዜ ገለጸ፤ (በ3፥8 ላይ የሙሴን ቃል እንደሚሰሙት እግዚአብሔር ቢያረጋግጥለትም እሱ ግን ፈቃደኛ አልሆነም)።

4፥2 *በትር፤* ምናልባት እረኞች የሚይዙት ዱላ ሳይሆን አይቀርም።

4፥3 *እባብ፤* የ7፥9-10 ማብ ይመ። የግብፅ ፈርዖኖች ልዑላን መሆናቸውን ለማሳየት፣ ከብረት የተሠሩ የእባብ ምስሎችን በራሶቻቸው በሚደፉአቸው ዘውዶች ላይ ያስቀርጹ ነበር።

4፥8 *ታምር፤* ሥልጣንን ለማሳየት የሚደረጉ መለኮታዊ ኹነቶች ወይም ክስተቶች ማረጋገጫ ይሆናሉ፤ (ኢሱ2፥12-13 ይመ)፤ ምስክር ይሆናሉ፣ (ኢሳ19፥19-20 ይመ)፤ ማስጠንቀቂያ ይሰጣሉ፣ (ዘኍ17፥10 ይመ) ወይም እምነትን ያጸናሉ። የ3፥12 ማብ ይመ።

*4፥10፤* ሙሴ ፈቃደኛ አለመሆኑን ለአራተኛ ጊዜ ገለጸ። *እኔ ኰልታፋና ንግግር የማልችል ሰው ነኝ፤* መናገር የማልችል ድዳ ነኝ ለማለት አይደለም፤ (ሐሥ 7፥22 ይመ)። ሙሴ በዚህ ቦታ ለማለት የፈለገው ለፈርዖን መልስ ለመስጠት አንደበተ ርቱዕ አይደለሁም ለማለት ነው፤ (6፥12 ይመ)። በ2ቆሮ 10፥10 ላይ ስለ ጳውሎስ የተነገረውን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ።

*4፥13፤* ሙሴ ፈቃደኛ አለመሆኑን ለአምስተኛና ለመጨረሻ ጊዜ ገለጸ።

4፥14 *የእግዚአብሔር ቍጣ በሙሴ ላይ ነደደ፤* ምንም እንኳ እግዚአብሔር "ለቍጣ የዘገየ" ቢሆንም፣ (34፥6)፣ እምቢተኛ ልጆቹን ለመቅጣት ግን ወደኋላ አይልም፤ (34፥7 ይመ)። *ሌዋዊው፤* በአሮን አመራር ሥር የሚሆኑት የእስራኤል ካህናት የሚወጡት ከሌዊ ነገድ ነው።

*4፥15-16፤* የ7፥1-2 ማብ ይመ።

4፥19 *ሰዎች ሁሉ ሞተዋልና፤* ቱትሞስ ሦስተኛን ጨምሮ ነው፤ (2፥15፡23 ይመ፤ እንዲሁም የመጽሐፉን መግቢያ ይመ)።

4፥20 *ልጆቹን፤* ጌርሳምንና (2፥22 ይመ)፤ አልዓዛርን

መመለስ ጀመረ፤ የእግዚአብሔርንም (ኤሎሂም) በትር በእጁ ይዞ ነበር።

[21]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፣ "ወደ ግብፅ በምትመለስበት ጊዜ በስጠሁህ ኀይል የምትሠራቸውን ታምራት ሁሉ በፈርዖን ፊት መፈጸም እንዳለብህ አትዘንጋ። እኔ ግን ሕዝቡን እንዳይለቅ ልቡን አደነድነዋለሁ። [22]ስለዚህ ለፈርዖን እንዲህ በለው፤ 'እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲህ ይላል፤ እስራኤል የበኵር ልጄ ነው፤ [23]"ያመልከኝ ዘንድ ልጄን ልቀቀው" ብዬህ ነበር፤ አንተ ግን እንዳይሄድ ከለከልኸው፤ ስለዚህ የበኵር ልጅህን እገድላለሁ።'"

[24]ሙሴ[a] በጕዞ ላይ በእንግዳ ማረፊያ ስፍራ ውስጥ ሳለ እግዚአብሔር (ያህዌ) አግ ኝቶት ሊገድለው ፈልጎ ነበር። [25]ሚስቱ ሲፓራ ግን ስለታም ባልጩት ወስዳ ልጇን ገረዘ ችው፤ በሸለፈቱ የሙሴን እግር በመን ካትም[b] "አንተ ለእኔ የደም ሙሽራዬ ነህ" አለችው። [26]ስለዚህም እግዚአብሔር (ያህዌ) ተወው፤ "አንተ የደም ሙሽራ ነህ" ያለ ችው በግርዛቱ ምክንያት ነው።

[27]እግዚአብሔር (ያህዌ) አሮንን፣ "ሙሴን እንድታገኘው ወደ ምድረ በዳ ሂድ" አለው። እርሱም ሙሴን በእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ተራራ አገ ኘው፤ ሳመውም። [28]ሙሴም እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲናገር የላከውን ቃል በሙሉና እን ዲፈጽማቸው ስላዘዘው ታምራዊ ምልክቶች ሁሉ ለአሮን ነገረው።

[29]ሙሴና አሮን ሄዱና የእስራኤልን ሕዝብ አለቆች በአንድነት ሰበሰቡ፤ [30]አሮንም እግ ዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ የነገረውን ቃል በሙሉ ነገራቸው። ታምራቱንም በሕዝቡ ፊት አደረገ። [31]ሕዝቡም አመኑ፣ እግዚአ ብሔር (ያህዌ) ስለ እነርሱ የሚገደው መሆኑ ንና መከራቸውን ማየቱን በሰሙ ጊዜ ተን በረከኩ፤ በስግደትም አመለኩ።

4፥21 ዘፀ3፥19፡20፤ 7፥3፡13፤8፥15፡32፤ 9፥12፡17፡35፤10፥1፡ 20፡27፤11፥10፤14፥4 ፡8፤ዘዳ2፥30፤ኢሱ11፥ 20፤1ሳሙ6፥6፤መዝ 105፥25፤ኢሳ6፥10፤ 63፥17፤ዮሐ12፥40፤ ሮሜ9፥18
4፥22 ዘፍ10፥15፤ ዘዳ32፥6፤ኢሳ9፥6፤ 63፥16፤64፥8፤ ኤር3፥19፤31፥9፤ ሆሴ11፥1፤ሚል2፥ 10፤ሮሜ9፥4፤ 2ቆሮ6፥18
4፥23 ዘፍ49፥3፤ ዘፀ3፥18፤5፥1፤7፥16፤ 11፥5፤12፥12፡29፤ ዘኍ8፥17፤33፥4፤ መዝ78፥51፤105፥ 36፤135፥8፤136፥10
4፥24 ዘኍ22፥22
4፥25 ዘፀ2፥21፤ዘፍ 17፥14፤ኢሱ5፥2፡3
4፥27 ዘፍ27፥27፤ 29፥13፤ዘፀ3፥1
4፥28 ቍ16
4፥29 ዘፀ3፥16
4፥30 ቍ8
4፥31 ዘፍ16፥11፤ 24፥26፤ዘፀ3፥18፤ 2፥25
5፥1 ዘፀ4፥23፤3፥18
5፥2 ዘፀ3፥19፤ መሳ2፥10፤ኢዮ21፥ 15፤ሚል3፥14
5፥3 ዘፍ30፥36፤ ዘሌ26፥25፤ዘኍ14፥ 12፤ዘዳ28፥21፤ 2ሳሙ24፥13
5፥4 ዘፀ1፥11፤ 6፥6-7
5፥5 ዘፍ12፥2
5፥6 ዘፍ15፥13
5፥7 ዘፍ11፥3
5፥8 ቍ14፡17፡18፤ ዘፀ10፥11
5፥10 ቍ13፤ ዘፀ1፥11

## ጭድ አልባ ሸክላ

**5** ከዚህ በኋላ ሙሴና አሮን ወደ ፈርዖን ሄደው፣ "የእስራኤል ስምላክ እግዚአብሔር (ኤሎሂም ያህዌ) 'በምድረ በዳ በዓል እንዲያደርግ ልኝ ሕዝቤን ልቀቅ' ይላል" አሉት።

[2]ፈርዖንም "እንድታዘዘውና እስራኤልን እንድለቅለት ለመሆኑ ይህ እግዚአብሔር (ያህዌ) ማነው?" እግዚአብሔርን (ያህዌ) አላው ቅም፤ እስራኤልንም አለቅም" አለ።

[3]እነርሱም፣ "የዕብራውያን ስምላክ (ኤሎሂም) ለእኛ ተገልጦልናል፤ የሦስት ቀን መንገድ ወደ ምድረ በዳው ተጕዘን ለአምላካችን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መሥዋዕት እንድንሠዋ ፍቀድልን፤ አለዚያ ግን በመቅሠፍት ወይም በሰይፍ ይመታናል" አሉት።

[4]የግብፅ ንጉሥም፣ "እናንተ ሙሴና አሮን፤ ለምንድነው ሕዝቡን ሥራ የምታስ ፈቱት? በሉ እናንተም ወደየሥራችሁ ተመ ለሱ!" [5]ፈርዖንም፣ "እነሆ፤ አሁን የምድ ሪቱ ሕዝብ እጅግ ብዙ ነው፤ እናንተም እንዳይሠሩ እያደረጋችኋቸው ነው" አለ።

[6]በዚያኑ ዕለት ፈርዖን ለባሪያ ተቈጣ ጣሪዎቹና ለሕዝቡ አለቆች እንዲህ ሲል ትእዛዝ ሰጠ፤ [7]"ለጡብ ሥራ የሚያስፈል ጋቸውን ጭድ ካለበት ቦታ ሄደው ራሳ ቸው ያምጡ እንጂ ከእንግዲህ እናንተ እን ዳታቀርቡላቸው። [8]ሆኖም ቀድሞ በሚያቀ ርቡት ሸክላ ልክ ሠርተው እንዲያቀርቡ አድርጓቸው። የሥራ ድርሻቸውን አትቀ ንሱ። ሰነፎች ናቸው፤ 'ሄደን ለአምላካችን መሥዋዕት እንሠዋ' የሚሉትም ለዚህ ነው። [9]ለሐሰት ወሬ ስፍራ ሳይሰጡ ተግተው እንዲሠሩ ሥራውን አክብዱባቸው።"

[10]ከዚያም የባሪያ ተቈጣጣሪዎቹና አለ

[a]24 ወይም፣ የሙሴ ልጅ ሊሆን ይችላል። ዕብራይስጡ፣ እርሱ ይላል።
[b]25 ወይም ወደ ሙሴ እግር በመቅረብም ሊባል ይችላል።

ነው። የሁለተኛው ልጅ ስም 18፥4 ላይ እስከምንደርስ ባይጠ ቀስም ቀደም ብሎ ተወልዶአል።

4፥21 *ታምራት፤* የ3፥20 ማብ ይመ። *ልቡን አደነድነ ዋለሁ፤* በዘፀአት መጽሐፍ ውስጥ እግዚአብሔር የፈርዖንን ልብ እንደሚያደነድን ዘጠኝ ጊዜ ተነግሮአል፤ (እንዲሁም 7፥3፤ 9፥12፤ 10፥1፡20፡27፤ 11፥10፤ 14፥4፡8፤ሮሜ 9፥17-18 እና ማብ ይመ)፤ ፈርዖን የራሱን ልብ እንደሚያደነድን ደግሞ ዘጠኝ ጊዜ ተገ ልጾአል፤ (7፥13-14፡22፤ 8፥15፡19፡32፤ 9፥7፡34-35)። የመጀመሪ ያዎቹ አምስት መቅሠፍቶች በግብፃውያን ላይ የወረዱት ፈርዖን ራሱ ልቡን በማደንደኑ ነው። እግዚአብሔር ለሙሴ በተናገረው መሠረት፣ (9፥12 ይመ) በግብፃውያን ላይ መቅሰፍቱን ማውረድ ያላቋረጠው ፈርዖን ከእምቢተኛነቱ ባለመመለሱ ነው (ሮሜ 1፥24-28 ይመ)።

4፥22 *የበኵር ልጄ፤* እስራኤል ከእግዚአብሔር ጋር ያላ ትን ልዩ ግንኙነት የሚገልጽ ምሳሌያዊ አነጋገር ነው፤ (ኤር 31፥9፤ ሆሴ 11፥1 ይመ)። *ልጄን፤* በሆሴ 11፥1 ላይ መላውን የእስራኤል ሕዝብ ለማመልከት ገብቶአል።

4፥23 *የበኵር ልጅህን እገድላለሁ፤* ዐሥረኛውን መቅሠ ፍት የሚያመለክት ነው፤ (11፥5፤12፥12 ይመ)።

4፥24 *በእንግዳ ማረፊያ ስፍራ፤* ምናልባት መንገደኞች ምሽቱን የሚያሳልፉበትና ውሃ ያለበት ስፍራ ይሆናል። *እግዚ አብሔር ... ሊገድለውም ፈለገ፤* እግዚአብሔር ሙሴን ሊገድ ለው የፈለገው ልጁን ስላልገረዘ ነው፤ (ዘፍ 17፥9-14 ይመ)።

4፥25 *ሲፓራ ... ልጇን ገረዘችው፤* ሲፓራ፣ እግዚአብሔር በሙሴ እንዳልተደሰተ ስታይ፣ የልጇን ሸለፈት ወዲያውኑ ገረዘች። *ባልጩት፤* ከብረት የሚሠሩ መሣሪያዎች በዚህው ቢኖሩም፣ ባልጩት ለመግረዣ ጥቅም ላይ ይውል ነበር፤ ይህ የሆነው ምናልባት በወቅቱ ከነበሩት የብረት መሣሪያዎች ይልቅ፣ ባልጩት የበለጠ ስለት ያለው ስለሆነና ለቀዶ ሕክምናም ብቁ መሣሪያ በመሆኑ ነው (ኢሱ 5፥2 እና ማብ ይመ)።

4፥26 *የደም ሙሽራ፤* ምንም እንኳ በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ የሚኖሩ ሕዝቦች ግዝረትን ለተለያየ ምክንያት ቢጠ ቀሙበትም፣ ሲፓራ ልጇን በመግረዟ ሳታፍር አልቀረችም።

4፥30 *አሮንም እግዚአብሔር ለሙሴ የነገረውን ቃል ሁሉ ተናገረ፤* የ7፥1-2 ማብ ይመ።

5፥1 *ፈርዖን፤* የ3፥10 ማብ ይመ።

*5፥3፤* 3፥18 እና ማብ ይመ። ግብፃውያን ሳያዩአቸው መሥዋዕት የሚያቀርቡበት ምክንያት በ8፥26 ላይ ተገልጾአል፤ (የዘፍ 43፥32 ማብ ይመ)።

5፥6 *ለባሪያ ተቈጣጣሪዎቹና ለሕዝቡ አለቆች፤* ምናልባት በ1፥11 ላይ "አስገባሪዎች" ከሚለው ጋር አንድ ነው፤ (ማብ እዚያው ይመ)። *አለቆችን፤* እስራኤላውያን፣ አለቆችን እንዴት እንደሚሾሙና ሥራቸውም ምን እንደ ሆነ፤ በቍ 14-16 ላይ ተገልጾአል።

5፥7 *ገለባ፤* ተቀረጣጥፎ ከሸክላ ጭቃ ጋር ከተደባለቀ በኋላ ጡቦችን ለማያያዝ ያገለግላል።

5፥9 *ወሬ፤* እስራኤላውያን ልቀቀን የሚሉት ውሸታቸውን ነው በማለት ፈርዖን ደመደመ።

ቆቹ ወጥተው ለሕዝቡ:- "ፈርዖን የሚለው ይህ ነው፤ 'ከእንግዲህ ጭድ አልሰጣችሁም፤ [11]ሂዱና የራሳችሁን ጭድ ከየትም ፈልጋችሁ አምጡ፤ የሥራ ድርሻችሁ ግን ከቶ አይቀነስም'" አሉ። [12]ስለዚህም ሕዝቡ በጭድ ፈንታ ገለባ ለመሰብሰብ በግብፅ ምድር ሁሉ ተሰማሩ።

[13]የባሪያ ተቈጣጣሪዎቹም "በየዕለቱ መሥራት የሚገባችሁ ሥራ ቀድሞ ጭድ ስናቀርብላችሁ ከምትሠሩት ሥራ ማነስ የለበትም" እያሉ ያጣድፏቸው ነበር። [14]የሥራው የቅርብ ኀላፊዎች ተደርገው በፈርዖን የባሪያ ተቈጣጣሪዎች የተመደቡት እስራኤላውያንም፣ "የትናንቱንም ሆነ የዛሬውን ሸክላ ሥራ ድርሻችሁን እንደ ቀድሞው ለምን አላሟላችሁም?" እየተባሉ ይጠየቁና ይገረፉ ነበር።

[15]ከዚያም ሥራውን በቅርብ ሆነው የሚቈጣጠሩት እስራኤላውያን ኀላፊዎች ፈርዖን ፊት ቀርበው እንዲህ ሲሉ አቤቱታ አቀረቡ፤ "እኛን ባሮችህን እንደዚህ የምታደርገን ለምንድን ነው? [16]ለእኛ ለባሮችህ ጭድ ሳያቀርቡልን ሸክላ ሥሩ ይሉናል፤ ጥፋቱ የገዛ ሰዎችህ ሆኖ ሳለ እኛ ባሮችህ ግን እንገረፋለን።"

[17]ፈርዖንም እንዲህ አለ፤ "ልግመኞች! እናንተ ልግመኞች! እየደጋገማችሁ እንሂድ 'ለእግዚአብሔር (ያህዌ) እንሠዋ' የምትሉት ለዚህ ነው። [18]በሉ አሁንም ወደ ሥራችሁ ተመለሱ፤ ምንም ጭድ አይሰጣችሁም፤ ያም ሆኖ ግን የተመደበላችሁን ሸክላ ማምረት አለባችሁ።"

[19]እስራኤላውያን ኀላፊዎችም፣ "በየቀኑ የምትሠሩት ሸክላ ቍጥሩ ቀድሞ ከሚሠራው ሸክላ ማነስ የለበትም" ተብሎ ሲነገራቸው ችግር ላይ መውደቃቸውን ተረዱት። [20]ከፈርዖን ዘንድ እንደተመለሱ ሲጠብቋቸው የነበሩትን ሙሴንና አሮንን አግኝተው፣ [21]"እግዚአብሔር (ያህዌ) ይይላችሁ፤ ይፍረድባችሁም ፈርዖንና ሹማምንቱ እንዲጠየፉን አደረጋችሁ፤ እንዲገድሉን በእጃቸው ሰይፍ ሰጣችኋቸው" አሏቸው።

### እግዚአብሔር (ኤሎሂም) እንደሚታደግ ተስፋ ሰጠ

[22]ሙሴም ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ተመልሶ፦ "አቤቱ ጌታ ሆይ፤(አዶናይ) በዚህ ሕዝብ ላይ መከራ ያመጣኸው ለምንድን ነው? የላክኸኝ ለዚሁ ነው? [23]በአንተ ስም እናገር ዘንድ ወደ ፈርዖን ከሄድሁበት ጊዜ ጀምሮ፣ እርሱ በዚህ ሕዝብ ላይ፣ አበሳ አምጥቶ አል፤ አንተም ሕዝብህን ከቶ አልታደግኸውም" አለው።

6 ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "አሁን በፈርዖን ላይ የማደርገውን ታያለህ፤ ከኀያሉ እጄ የተነሣ እንዲሄዱ፣ ይለቃቸዋል፤ ከኀያሉም እጄ የተነሣ ከአገሩ ያስወጣቸዋል" አለው።

[2]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) ሙሴን አለው፤ "እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) ነኝ። [3]ሁሉን የሚችል አምላክ[ሀ] (ኤሎሂም) ሆኜ ለአብርሃም፣ ለይስሐቅ፣ ለያዕቆብ ተገለጥሁ ላቸው፤ ነገር ግን እግዚአብሔር (ያህዌ) በተባለው ስሜ[+] ራሴን አልገለጥሁላቸውም።[‡] [4]በእንግድነት የሚኖሩባትን የከነዓንን ምድር እንድሰጣቸው ከእነርሱ ጋር ቃል ኪዳን ገብቻለሁ። [5]ደግሞም በግብፃውያን ሥር በባርነት ሆነው ያስሙትን የእስራኤላውያንን የሥቃይ ድምፅ ሰምቻለሁ ኪዳኔንም አስታውሻለሁ።

[6]"ስለዚህ ለእስራኤላውያን እንዲህ በላቸው፤ 'እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) ነኝ፤ ከግብፃውያን ቀንበር አወጣችኋለሁ። ለእነርሱ ባሪያ ከመሆን ነጻ አወጣችኋለሁ፤ በተዘረጋች ክንድና በታላቅ ፍርድ እቤዣችኋለሁ። [7]የራሴ ሕዝብ አደርጋችኋለሁ፤ እኔም አምላክ (ኤሎሂም) እሆናችኋለሁ ከግብፃውያን ቀንበር ያላቀቅኋችሁ እኔ እግዚአብሔር አምላክ (ያህዌ ኤሎሂም) መሆኔንም ታውቃላችሁ። [8]ከዚያም

5፥11 ቍ19
5፥14 ቍ16፤ ኢሳ10፥24
5፥17 ቍ8
5፥18 ዘፍ15፥13
5፥21 ዘፍ16፥5፤ 34፥30፤ዘፀ1፥13፤ 14፥11፤16፥3፤ ዘኍ14፥3፤20፥3
5፥22 ዘኍ11፥11፤ ዘዳ1፥12፤ኢሱ7፥7
5፥23 ኤር4፥10፤ 20፥7፤ሕዝ14፥9
6፥1 ዘፀ3፥20፤ 11፥1፤12፥31፡33፡39 ዘዳ5፥15
6፥2 ቍ6፡7፡8፡29፤ ዘፀ3፥14፡15፤7፥5፡ 17፤8፥22፤10፥2፤ 12፥12፤14፥4፡18፤ 16፥12፤ዘሌ11፥44፤ 18፥21፤20፥7፤ ኢሳ25፥3፤41፥20፤ 43፥11፤ 49፥23፤ 60፥16፤ሕዝ13፥9፤ 25፥17፤36፥38፤ 37፥6፡13፤ኢል2፥27
6፥3 ዘፍ17፥1፤ዘፀ 3፥14፡15፤2ሳሙ7፥2 6፤መዝ48፥10፤61፥5፤ 68፥4፤83፥18፤99፥3፤ ኢሳ52፥6፤ዮሐ8፥58
6፥4 ዘፍ6፥18፤ 12፥7፤15፥18፤17፥8፤ ሐሥ7፥5፤ሮሜ 4፥13፤ገላ3፥16፤ ዕብ11፥8-10
6፥5 ዘፍ 9፥15፤ ዘፀ2፥23፤ሐሥ7፥34፤
6፥6 ቍ7፤ ዘፀ3፥8፡19፡20፤ 12፥17፡51፤15፥13፤ 16፥16፤18፥1፤ 19፥1፤20፥2፤29፥46፤ ዘሌ22፥33፤26፥13፤ ዘዳ6፥12፤7፥8፤ 9፥26፤1ዜና17፥21፤ ኢዮ19፥25፤ መዝ9፥16፤19፥14፤ 34፥22፤74፥2፤ 77፥15፤81፥10፤ 105፥27፤107፥2፤ 136፥11፤ኢሳ29፥22፤ 35፥9፤43፥1፤44፥23፤ 48፥20፤ኤር2፥6፤ 15፥21፤31፥11፤ 32፥21፤50፥34፤ ሆሴ13፥4፤ አሞ2፥10፤ሚክ6፥4፤ሐሥ13፥17
6፥7 ቍ2፤ ዘፍ17፥7፤ዘፀ34፥9፤ 1ነገ20፥13፡28፤ኢሳ43፥10፤48፥7፤ሕዝ11፥19-20፤ 39፥6፤ኢል3፥17፤ ሮሜ9፥4

[ሀ]3 ዕብራይስጡ፣ ኤልሻዳይ ይለዋል።
[+]3 የዘፀ 3፥15 ማብ ይመ
[‡]3 ወይም እግዚአብሔር በተባለው ስሜ ራሴን አልገለጥሁላቸውምን? ተብሎ ሊተረጐም ይቻላል።

5፥21 *እግዚአብሔር ይይላችሁ፤ ይፍረድባችሁም፤* ዘፍ 16፥5፤ 31፥49 እና ማብ ይመ።

6፥1 *አሁን፤* ብዙ ሳይዘገይ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ይፈርዳል ለማለት ነው።

6፥2 *እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤* ይህ ዐረፍተ ነገር በዚህ ምዕራፍ ውስጥ አራት ጊዜ ተጠቅሶአል፤ የተጠቀሰውም (1) የመልእክቱን ዐቢይ ሐሳብ ለማስተዋወቅ፤ (2) እግዚአብሔር ሕዝቡን እንደሚቤዥ ለማረጋገጥ፣ (ቍ 6)፤ (3) እግዚአብሔር እስራኤልን እንደ ራሱ ልጅ ለማድረግ ማሰቡን ለማመልከት፣ (ቍ7)፤ (4) እግዚአብሔር በገባው ቃል መሠረት የተስፋዪቱን ምድር እንደሚያወርሳቸው ለማስታወቅና መልእክቱን ለማጠቃለል ነው (ቍ8)።

6፥3 *ሁሉን የሚችል አምላክ፤* የዘፍ 17፥1 ማብ ይመ። *እግዚአብሔር በተሰኘው ቅዱስ ስሜ ... አልተገለጥሁላቸውም፤* ይህ ማለት የእስራኤል አባቶች፣ ያህዌ የሚለውን ስም ጨርሶ አያውቁም ነበር ማለት አይደለም፤ ነገር ግን የስሙ ሙሉ ትርጕም ይኸውም ሕዝቡን የሚታደግ ስም እንደ ሆነ አያውቁም ነበር (የቍ 6 ማብ እና ዘፍ 2፥4 ይመ)። ይህ ስም፣ ሕዝቡን የሚታደግ ስም እንደ ሆነ ሙሉ በሙሉ የሚረዱት፣ ከግብፅ የወጡት እስራኤላውያንና ልጆቻቸው ብቻ ናቸው። *አልተገለጥሁላቸውም፤* ይህ ቃል "መታወቅ" የሚል ትርጕም ያለው ሲሆን ስለ መቅሰፍቶቹ በተነገረው ታሪክ ውስጥ (ቍ 7፤ 7፥17፤ 8፥10፡22፤ 9፥14፡29፥19፥2፤ 11፥7 ይመ)፤ እንዲሁም ከራሱ ከግብፅ መውጣት ታሪክ ጋር በተደጋጋሚ ተጠቅሶ ይገኛል (14፥4፡18፤ 16፥6፡8፡12፤18፥11 ይመ)።

6፥5 *አስታውሻለሁ፤* የዘፍ 8፥1 ማብ ይመ።

6፥6 *አወጣችኋለሁ ... እቤዣችኋለሁ ... እታደጋችኋለሁ፤* እነዚህ ግሦች ያህዌ የሚለው ስም የያዘውን ትክክለኛ ትርጕም በግልጽ ይናገራሉ፤ ያህዌ ሕዝቡን የሚቤዥ ነው፤ (የቍ3 ማብ ይመ)። *በታላቅ ፍርድም፤* 7፥4 ይመ። የእግዚአብሔር ፍርድ መቤዠትን (ለእስራኤል) እንዲሁም ፍርድን (በግብፃውያን ላይ) ያካትታል።

6፥7-8 *ያላቀቅኋችሁ ... አመጣችኋለሁ፤* መቤዠት ማለት ከባርነትና ከስቃይ ነጻ መውጣት ማለት ብቻ ሳይሆን ነጻና ደስተኛ ሕዝብ ለመሆንም ነጻ መውጣት ማለት ነው።

6፥7 *የራሴ ሕዝብ አደርጋችኋለሁ፤ እኔም አምላክም እሆናችኋለሁ፤* እግዚአብሔር በሲና ተራራ ላይ የተናገረውን ቃል የሚያስታውስ ነው፤ (19፥5-6፤ እንዲሁም ኤር 31፥33 ይመ)።

ለአብርሃም፣ ለይስሐቅ፣ ለያዕቆብ እሰጣች ኋለሁ ብዬ ወደማልሁላቸው ምድር አመጣ ችኋለሁ፤ ርስት አድርጌ እሰጣችኋለሁ። እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) ነኝ።'"

[9]ሙሴ ይህን ለእስራኤላውያን ነገራ ቸው፤ ተስፋ ከመቍረጣቸውና ከአስከፊ እስ ራታቸው የተነሣ ግን አላዳመጡትም።

[10]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [11]"ሂድና ለግብፅ ንጉሥ ለፈርዖን እስራኤላውያን ከአገሩ እንዲወጡ ይፈቅድላቸው ዘንድ ንገረው።"

[12]ሙሴ ግን እግዚአብሔርን (ያህዌ)፣ "እስ ራኤላውያን ያልሰሙኝ፣ ፈርዖን እንዴት ይሰማኛል፤ እኔ ለራሴ ተብታባ ሰው ነኝ"[1] አለው።

## የሙሴና የአሮን የትውልድ መዝገብ

[13]በዚህ ሁኔታ እግዚአብሔር (ያህዌ) ስለ እስራኤላውያንና ስለ ግብፅ ንጉሥ ስለ ፈር ዖን ለሙሴና ለአሮን ነገራቸው፤ እስራኤላ ውያንንም ከግብፅ እንዲያወጡ አዘዛቸው።

[14]የየቤተ ሰቡ[2] አለቆች እነዚህ ነበሩ፤ የእስራኤል የበኵር ልጅ የሮቤል ልጆች፣ ሄኖኅ፣ ፈሉስ፣ አስሮን፣ ከርሚ፣ እነዚህ የሮቤል ነገድ ናቸው።

[15]የስምዖን ወንዶች ልጆች፣ ይሙኤል፣ ያሚን፣ኦሃድ፣ ያኪን፣ ጾሐርና የከነዓናዊቷም ልጅ ሳኡል ነበሩ። እነዚህ የስምዖን ነገድ አባቶች ናቸው።

[16]በትውልዳቸው መሠረት የሌዊ ወን ዶች ልጆች ስሞች እነዚህ ነበሩ፤ ጌድሶን፣ ቀዓትና ሜራሪ ናቸው፤ ሌዊ መቶ ሠላሳ ሰባት ዓመት ኖረ።

[17]የጌድሶን ወንዶች ልጆች በትውልዳ ቸው ሎቤኒና ሰሜኢ ነበሩ።

[18]የቀዓት ወንዶች ልጆች እንበረም፣ ይስዓር፣ ኬብሮንና ዑዝኤል ነበሩ፤ ቀዓት መቶ ሠላሳ ዓመት ኖረ።

[19]የሜራሪ ወንዶች ልጆች ሞሖሊና ሙሲ ነበሩ። በትውልዳቸው መሠረት የሌዋ ነገዶች እነዚህ ናቸው።

[20]እንበረም የአጎቱን እናት ዮካብድን አገባ፤ እርሷም አሮንንና ሙሴን ወለደችለት። እንበረም መቶ ሠላሳ ሰባት ዓመት ኖረ።

[21]የይስዓር ወንዶች ልጆች፣ ቆሬ፣ ናፌግና ዝክሪ ነበሩ።

[22]የዑዝኤል ወንዶች ልጆች፣ ሚሳኤል፣ ኤልዳፋንና ሥትሪ ነበሩ።

[23]አሮንም የአሚናዳብን ልጅ፣ የነአሶንን እኅት ኤልሳቤጥን አገባ፤ እርሷም ናዳብንና አብዩድን፣ አልዓዛርንና ኢታምርን ወለደ ችለት።

[24]የቆሬ ወንዶች ልጆች፣ አሴር፣ ሕል ቃናና አብያሳፍ ነበሩ፤ እነዚህ የቆሬ ነገድ ጐሣ ናቸው።

[25]የአሮን ልጅ አልዓዛር ከፉትኤል ሴት ልጆች አንዷን አገባ፤ እርሷም ፊንሐስን ወለደችለት፤ እነዚህ እንደየነገዳቸው የሌዋ ውያን ጐሣዎች አለቆች ነበሩ።

[26]እግዚአብሔር (ያህዌ) "እስራኤላውያንን በየሰራዊታቸው ከግብፅ አውጡ" ብሎ የነገ ራቸው እነዚህኑ አሮንንና ሙሴን ነበር።

[27]ስለ እስራኤላውያን ከግብፅ መው ጣት፣ የግብፅን ንጉሥ ፈርዖንን ያናገሩትም እነዚሁ ነበሩ።

[28]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን በግብፅ በተናገረው ጊዜ፣ [29]እንዲህ አለው፤ "እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) ነኝ፤ የነገርሁህን ሁሉ ለግብፅ ንጉሥ ለፈርዖን ንገረው።"

[30]ሙሴ ግን እግዚአብሔርን (ያህዌ) እንዲህ አለው፤ "ፈርዖን ምን ብሎ ይሰማኛል? አን ደበቴ ኮልታፋ ነው።"

**7** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "ልብ በል፤ እኔ አንተን ለፈርዖን እንደ ኤሎሂም (አምላክ) አድርጌሃለሁ፤ ወንድምህ አሮ ንም ያንተ ነቢይ ይሆናል። [2]እኔ የማዝዝህን ሁሉ ትናገራለህ፤ ወንድምህ አሮንም እስራ ኤላውያንን ከአገሩ እንዲወጡ ይለቃቸው ዘንድ ለፈርዖን ይነግረዋል። [3]እኔ ግን የፈር ዖንን ልብ አደነድናለሁ፤ ታምራዊ ምልክቶ ችንና ድንቆችን በግብፅ ላይ በብዛት ባደ

6፥8 ዘፍ12፥7፤14፥22፤26፥3፥8፤ዘሌ18፥21፤መዝ136፥21-22፤ኤር11፥5፤ሕዝ20፥6፤ራእ10፥5-6
6፥9 ዘፍ34፥30፤ዘፀ2፥23
6፥11 ቍ29፤ዘፀ3፥18
6፥12 ዘፀ3፥18፤4፥10
6፥13 ዘፀ3፥10
6፥14 ዘፍ29፥32፤ዘፀ13፥3፤ዘኍ1፥1፤26፥4
6፥15 ዘፍ29፥33
6፥16 ዘፍ29፥34፤46፥11፤ዘኍ3፥17፤ኢሱ21፥7፤1ዜና6፥1:16
6፥17 ዘኍ3፥18፤1ዜና6፥17
6፥18 ዘኍ3፥19፤27፤1ዜና6፥2:18፤23፥12
6፥19 ዘኍ3፥20:33፤1ዜና6፥19:23፥21
6፥20 ዘፀ2፥1-2፤ዘኍ26፥59፤1ዜና23፥13
6፥21 1ዜና6፥38
6፥22 ዘሌ10፥4፤ዘኍ3፥30፤1ዜና15፥8፤2ዜና29፥13
6፥23 ዘፀ24፥1፤28፥1፤ዘሌ10፥1:6:12:16፤ዘኍ1፥7፤2፥3፥3፥2:32፤4፥28፤16፥37:39፤26፥60፤ዘዳ10፥6፤ኢሱ14፥1፤ሩት4፥19:20፤1ዜና6፥3፤24፥1፤1ዜና2፥10፤6፥22:37፤ማቴ1፥4
6፥24 ቍ21፤ዘኍ16፥1፤
6፥25 ዘኍ25፥7:11፤31፥6፤ኢሱ24፥33፤መዝ106፥30
6፥26 ዘፀ3፥10፤7፥4፤12፥17:41:51
6፥27 ዘፀ5፥1፤ዘኍ3፥1፤መዝ77፥20
6፥29 ቍ2
6፥30 ዘፀ3፥11
7፥1 ዘፀ4፥15:16፤ሐሥ14፥12
7፥3 ዘፀ3፥20፤4፥21፤10፥1፤

[1] 12 ዕብራይስጡ በዚህ ስፍራና ቍ 30 ላይ፣ ያልተገረዘ ከንፈር ይላል

[2] 14 በዚህ ስፍራና በቍ 25 ላይ፣ ያለው ቤተ ሰብ የዕብራይስጥ ቃል ከጐሣም የበለጠ ነው።

6፥8፤ ዘፍ 22፥15-17 ይመ። *ወደ ማልሁላቸው፤* የዘፍ 14፥22 ማብ ይመ።

6፥12 *ተብታባ ሰው ነኝ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

6፥13 *ለሙሴና ለአሮን፤* በቍ 14-25 ላይ የተጠቀሰው የትውልድ ሐረግ፣ ሙሴና አሮን የማን ልጆች እንደሆኑ ይናገራል። ሙሴና አሮን ከሦስተኛው ነገድ ቢሆኑም፣ እዚህ ላይ ስማቸው የተጠቀሰው ከያዕቆብ 12 ልጆች መካከል የሦስቱ (የሮቤል፣ የስ ምዖንና የሌዊ) ብቻ ነው።

6፥16 *ሜራሪ፤* ይህ ስም የግብፃውያን ስም ነው፤ እንደ ከፉትኤልና ፊንሐስ (ቍ 25 ይመ) ይህም እንደ ራሱ እንደ ሙሴ (የ2፥10 ማብ ይመ)። *የሌዊም የሕይወት ዘመን መቶ ሠላሳ ሰባት ዓመት ነው፤* ቍ 18:20 ይመ። በብሉይ ኪዳን አንድ ሰው በሕይወት የኖረበት ዘመን የሚጠቀሰው ዕድሜው ከመቶ ዓመት የበለጠ እንደሆነ ነው።

6፥20 *እንበረም… አሮንንና ሙሴን፤* ዓምራምና ዮኬቤድ የአሮንና የሙሴ አባቶች እንጂ፣ ወላጆች አይደሉም የሚል አስተ ያየት አለ። የዓምራም አባት ቀዓት (ቍ 18 ይመ)፤ የተወለደው ያዕቆብ ወደ ግብፅ ከመውረዱ በፊት ነው፤ (ዘፍ 46፥11 ይመ)፤ እስራኤላውያን በግብፅ ምድር 430 ዓመት ኖረዋል፤ (12፥40-41 ይመ)። እስራኤላውያን ከግብፅ ሲወጡ ሙሴ የ80 ዓመት ሰው በመሆኑ፤ (7፥7 ይመ)፤ ሙሴ የተወለደው ቀዓት ከተወለደ ከ350 ዓመት በኋላ ነው፤ ስለዚህ ቀዓት የሙሴ አያት ሊሆን አይችልም፤ (ቍ 18 ይመ)። እንግዲህ እንበረም የሙሴ አባት አይደለም ማለት ነው፤ "ወለደ" ለሚለው ቃል የገባው የዕብራ ይስጡ ግሥ አንዳንድ ጊዜ በዘፍጥረት 10 ላይ ካለው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይ ትርጕም አለው፤ (በዘፍ 10፥8 ላይ ቃሉ "የ … አባት" ተብሎ ተተርጕሞአል)። *ዮኬቤድ፤* የስሙ ትርጕም "እግዚአብሔር ክብር ነው" ማለት ነው። *አሮንንና ሙሴን፤* አሮን የመጀመሪያ ልጅ በመሆኑ፤ (7፥7 ይመ) ስሙ በቅድሚያ ተጠቅሶአል።

6፥30 *አንደበቴ ኮልታፋ፤* ቍ 12 እና የ4፥10 ማብ ይመ።

*7፥1-2፤* እግዚአብሔር በነቢያቱ በኩል ቃሉን ለሕዝቡ እንደሚያስተላልፍ ሁሉ፣ ሙሴም የእግዚአብሔርን ቃል በአሮን በኩል ለፈርዖን አስተላለፈ። የነቢያት ተልዕኮ በእግዚአብሔር ምትክ የእግዚአብሔርን ቃል መናገር ነው። እርሱ የእግዚአብሔር "አፍ" ነበር (4፥15-16)።

7፥3 *አደነድናለሁ፤* የ4፥21ን ማብ ይመ። *ታምር፤* የ3፥12፤

ርግም እንኳ፣ አይሰማችሁም:: [4]ከዚያም እጄን በግብፅ ላይ አደርጋለሁ፤ በኀያል ፍርድም ሰራዊቴን፣ ሕዝቤን እስራኤላውያንን አወጣለሁ፤ [5]እጄን በግብፅ ላይ ስዘረጋና እስራኤላውያንንም ከዚያ ሳወጣ፣ ግብፃውያን እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) መሆኔን ያውቃሉ::"

[6]ሙሴና አሮን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደ አዘዛቸው አደረጉ:: [7]ፈርዖንን ባነጋገሩበት ጊዜ ሙሴ ዕድሜው ሰማንያ ዓመት፣ አሮን ደግሞ ሰማንያ ሦስት ነበር::

## የአሮን በትር እባብ ሆነች

[8]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፣ [9]"ፈርዖን፣ 'ታምር አሳዩኝ' ባላችሁ ጊዜ፣ አሮንን እንዲህ በለው፤ 'በትርህን ውሰድና በፈርዖን ፊት ጣላት፤' ከዚያም እባብ ትሆናለች::"

[10]ስለዚህ ሙሴና አሮን ወደ ፈርዖን ሄደው *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዳዘዛቸው አደረጉ:: አሮን በትሩን በፈርዖንና በሹማምንቱ ፊት ጣላት፤ እባብም ሆነች:: [11]ከዚያም ፈርዖን ጠቢባኑንና መተተኞቹን ጠራ፤ የግብፅ አስማተኞችም በድብቅ ጥበባቸው ያንኑ አደረጉ፤ [12]እያንዳንዱ የያዛትን በትር ጣለ፤ እባብም ሆነች:: ነገር ግን የአሮን በትር የእነርሱን በትሮች ዋጠች:: [13]ሆኖም የፈርዖን ልብ ደነደነ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ተናግሮ እንደነበረውም አላዳመጣቸውም::

## የደም መቅሠፍት

[14]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "የፈርዖን ልብ ደነደነ፤ ሕዝቡን ለመልቀቅ አልፈቀደም:: [15]ወደ ውሃው በሚሄድበት ጊዜ ማልደህ ወደ ፈርዖን ሂድ፤ እንድታገኘውም በዐባይ ዳር ተጠባበቅ፤ ወደ እባብ ተለውጣ የነበረችውንም በትር በእጅህ ያዝ:: [16]ከዚያም እንዲህ በለው፤ 'የዕብራውያን አምላክ *እግዚአብሔር* (ኤሎሂም ያህዌ) "ሕዝቤ በምድረ በዳ ያመልኩኝ ዘንድ እንዲሄዱ ልቀቃቸው፤" ብዬ እንድነግርህ ላከኝ፤ አንተ ግን እስካሁን ድረስ እሺ አላልህም:: [17]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚለው ይህ ነው፤ "እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደሆንሁ በዚህ ታውቃለህ፤ እይ በዚህች በእጄ በያዝኳት በትር የዐባይን ውሃ እመታለሁ:: ወደ ደምም ይለወጣል:: [18]በዐባይ ወንዝ ውስጥ ያለው ዓሣ ይሞታል፤ ወንዙ ይከረፋል፤ ግብፃውያንም ውሃውን መጠጣት አይችሉም::' "

[19]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ "አሮንን፣ 'በትርህን ውሰድና በግብፅ ውሆች ላይ፣ ይኸውም በምንጮች፣ በቦዮች፣ በኩሬዎችና በውሃ ማጠራቀሚያዎች ላይ እጅህን ዘርጋ' ብለህ ንገረው፤ ወደ ደምም ይለወጣሉ:: ከእንጨትና ከድንጋይ በተሠሩ ውሃ መያዣዎች ውስጥም ሳይቀር በግብፅ ምድር ደም በየቦታው ይሆናል::"

[20]ሙሴና አሮን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደ አዘዛቸው አደረጉ:: እርሱም በንጉሡና በሹማምንቱ ፊት በትሩን አንሥቶ የዐባይን ወንዝ ውሃ መታ:: ውሃውም በሙሉ ወደ ደም ተለወጠ:: [21]በዐባይ ያሉት ዓሦች ሞቱ፤ ወንዙም ከመከርፋቱ የተነሣ ግብፃውያኑ ውሃውን ሊጠጡት አልቻሉም:: በግብፅ ምድር ሁሉ ደም ነበረ::

[22]የግብፅ አስማተኞች በድብቅ ጥበባቸው ተመሳሳይ ነገር አደረጉ፤ የፈርዖንም ልብ ደነደነ፤ ልክ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደ ተናገረው ሙሴንና አሮንን አልሰማቸውም:: [23]ተመልሶ ወደ ቤተ መንግሥቱ ገባ እንጂ ይህንን ከቁም ነገር አልቈጠረውም:: [24]ግብፃውያን ሁሉ የወንዙን ውሃ መጠጣት ባለመቻላቸው ውሃ ለማግኘት የዐባይን ዳር ይዘው ጒድጓድ ቈፈሩ::

[25]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ዐባይን ከመታ ሰባት ቀን አለፈ::

ሐሥ7፥36፤ ሮሜ9፥18
7፥4 ቍ13:16:22፤ ዘፀ8፥15:19፤9፥12፤ 11፥9፤3፥20፤6፥26፤ ሐሥ7፥36
7፥5 ዘፀ6፥2፤3፥20፤ መዝ138፥7፤ሕዝ6፥14፤25፥13
7፥6 ቍ2:10:20፤ ዘፍ6፥22
7፥7 ዘዳ31፥2፤ 34፥7፤ሐሥ7፥23:30
7፥9 ዘፀ4፥2-5፤ ዘዳ6፥22፤2ነገ19፥29፤ መዝ78፥43፤86፥17፤ 105፥27፤135፥9፤ ኢሳ7፥11፤37፥30፤ 38፥7-8፤55፥13፤ ዮሐ2፥11
7፥11 ቍ22፤ ዘፍ41፥8፤ዘፀ8፥7:18፤ 22፥18፤ዘዳ18፥10፤ 1ሳሙ6፥2፤2ነገ21፥6 ፤ኢሳ2፥6፤47፥12፤ ኤር27፥9፤ሚል3፥5፤ ማቴ24፥24፤ 2ጢሞ3፥8
7፥13 ቍ4፤ዘፀ 4፥21
7፥14 ቍ22፤ዘፀ 8፥15:32፤9፥7፤ 10፥1:20:27
7፥15 ዘፍ41፥1፤ዘፀ 8፥20
7፥16 ቍ4፤ዘፀ 3፥18
7፥17 ቍ19-21፤ ዘፀ4፥9፤6፥2፤14፥25፤ ራእ11፥6፤16፥4
7፥18 ቍ21:24፤ መዝ78፥44፤ ኢሳ19፥6
7፥19 ዘፀ4፥2፤ 14፥21፤2ነገ5፥11
7፥20 ቍ6፤ ዘፀ17፥5፤መዝ78፥ 44፤105፥29፤114፥3፤ ዕን3፥8
7፥22 ቍ11:13: 14፤ዘፍ41፥8፤ ዘፀ8፥19፤መዝ105፥ 28፤ማቴ24፥24
7፥24 ቍ18

የ4፥8ን ማብ ይመ::

7፥4 *በኀያል ፍርድም፤* የ6፥6 ማብ ይመ::

7፥7 *ሙሴ ዕድሜው ሰማንያ ዓመት፤* የ2፥11:15 ማብ ይመ::

7፥9-10 *እባብ፤* በዚህ ቦታ ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በ4፥3 ላይ ከተጠቀሰው ቃል የተለየ ነው፤ (መዝ 74፥13 ይመ):: ከዚህ ቃል ጋር ተዛማጅ የሆነ ቃል በሕዝ 29፥3 ላይ፣ ግብፅንና ነገሥታትን ለመወከል ገብቶአል::

7፥11 *ጠቢባኑንና መተተኞቹን፤* የ2ፍ 4፥8 ማብ ይመ:: በአይሁዳውያን ዘንድ በሚተረከው ታሪክ መሠረት፣ ሙሴን የተቃወሙት ሁለቱ አስማተኞች፣ ኢያኔስና ኢያንበሬስ የሚል ስም ተሰጥቶአቸዋል፤ (2ጢሞ 3፥8 ይመ፤ የኢያኔስ ስም ከሙት ባሕር በተገኙ ጽሑፎች ላይ ተጠቅሶአል):: እነርሱም በአስማታቸው እንደዚሁ አደረጉ፤ የግብፅ አስማተኞች ይህንን ያደረጉት በአጋንንት ኀይል ነው::

7፥12 *የአሮን በትር የእነርሱን በትሮች ዋጠች፤* እግዚአብሔር በፈርዖንና በግብፅ አማልክት ላይ ጌታና ልዑል መሆኑን ያመለክታል::

7፥13 *ልብ ደነደነ፤* የ4፥21 ማብ ይመ::

7፥14-10፥29 *የመጀመሪያዎቹ ዘጠኝ መቅሠፍቶች፣* ሦስት፣ ሦስት መቅሠፍቶችን በያዙ ሦስት ክፍሎች ሊመደቡ ይችላሉ፤ (7፥14-8፥19፤ 8፥20-9፥12፤ 9፥13-10፥29)፤ ከእያንዳንዱ ክፍል ውስጥ የሚገኙት የመጀመሪያዎቹ መቅሠፍቶች፣ (አንደኛው፣ አራተኛውና ሰባተኛው) ፈርዖን ጠዋት ጠዋት ወደ ዐባይ ወንዝ ሲወርድ የተሰጡ ማስጠንቀቂያዎች ናቸው፤ (ቍ 15፤8፥20፤ 9፥13 ይመ)::

7፥17 *በእጄ፤* በሙሴ እጅ ነው:: ውሃውም ወደ ደም ይለወጣል፤ መዝ 78፥44፤ 105፥29 ይመ:: እግዚአብሔር የፍጥረት ጌታ መሆኑን ያመለክታል::

7፥19 *በትሩን፤* አሮን ሙሴን ተክቶ እየሠራ ነው፣ (ቍ 17 ይመ):: *ከዕንጨትና ከድንጋይ በተሠሩት የውሃ ማጠራቀሚያ ዕቃዎች፤* አንዳንድ ሊቃውንት እንደሚሉት ግብፃውያን አማልክቶቻችን ከዕንጨት፣ ከሸክላና ከድንጋይ በተሠሩ ጣዖታትና ምስሎች፣ (ዘዳ 29፥16-17 ይመ) ላይ ያድራሉ ብለው ስለሚያምኑ፣ መቅሠፍቶቹ የግብፃውያን ሃይማኖት ከንቱ እንደ ሆነ ለማሳየት የተደረጉ ናቸው፤ (12፥12 ይመ)::

7፥20 *ዐባይ፤* የግብፅ ህልውና የተመሠረተው በዐባይ ወንዝ ላይ በመሆኑ በዐቢይ ወንዙ ሐጲ በሚል ስም ይመለክ ነበረ፤ ለዚህ አም ላክ የውዳሴ መዝሙር ተዘምሮለታል:: የቍ 19 ማብ ይመ::

7፥24 *የሚጠጣ ውሃ ለማግኘት ከወንዝ ዳር ጒድጓድ ቆፈሩ፤* ውሃው በወንዙ መፋሰሻ አጠገብ ባለው አሸዋማ ዐፈር ስለሚጣራ ለመጠጥ ውሃ ያገለግላል::

7፥25 *ሰባት ቀን አለፈ፤* መቅሠፍቱ በተከታታይ አልወረደም::

## የጓጉንቸር መቅሠፍት

8 ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ “ወደ ፈርዖን ዘንድ ሂደህ፣ እንዲህ በለው፤ ‘እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚለው ይህ ነው፤ “እኔን ያመልኩኝ ዘንድ ሕዝቤን ልቀቅ። [2]እነርሱን ለመልቀቅ እምቢ ብትል አገርህን ሁሉ በጓጉንቸር መቅሠፍት እመታዋለሁ። [3]ዐባይ በጓጉንቸሮች ይሞላል፤ ወጥተውም ወደ ቤተ መንግሥትህና ወደ መኝታ ክፍልህ፣ ወደ አልጋህም ወደ ሹማምንቶችህና ወደ ሕዝብህ ቤቶች፣ ወደ ምድጆችህና ወደ ቡሃቃዎችህ ይገባሉ። [4]ጓጉንቸሮቹ ወደ አንተና ወደ ሕዝብህ ወደ ሹማምንቶችህም ሁሉ ይመጡብችኋል።’ ”

[5]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፣ “አሮንን፣ ‘በትርህን ይዘህ በምንጮች፣ በቦዮችና በኩሬዎች ላይ እጅህን ዘርጋ፤ ጓጉንቸሮችም በግብፅ ምድር ላይ እንዲወጡ አድርግ’ ” በለው።

[6]አሮንም በግብፅ ውሆች ላይ እጁን ዘረጋ፤ ጓጉንቸሮችም ወጥተው ምድሪቱን ሸፈኑ። [7]ሆኖም ግን አስማተኞቹ በድብቅ ጥበባቸው ተመሳሳይ ነገር ሠሩ፤ እነርሱም በግብፅ ምድር ላይ ጓጉንቸሮች እንዲወጡ አደረጉ።

[8]ፈርዖንም ሙሴንና አሮንን አስጠርቶ እንዲህ አላቸው፤ ጓጉንቸሮቹን ከእኔና ከሕዝቤ ያርቅ ዘንድ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጸልዩልኝ፤ ከዚያም ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መሥዋዕትን ትሠዉ ዘንድ ሕዝቡ እንዲሄዱ እፈቅዳለሁ።

[9]ሙሴም ፈርዖንን፣ “በዐባይ ወንዝ ካሉት በቀር ከአንተና ከቤቶችህ ጓጉንቸሮቹ እንዲወገዱ ለአንተ፣ ለሹማምንቶችህና ለሕዝብህ የምንፀልይበትን ጊዜ እንድትወስን ለአንተ ትቼዋለሁ” አለው።

[10]ፈርዖንም፣ “ነገ ይሁን” አለው። ሙሴም እንዲህ ብሎ መለሰ፤ “እንደ አምላካችን እንደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ያለ ማንም እንደ ሌለ ታውቅ ዘንድ አንተ እንዳልኸው ይሆናል። [11]ጓጉንቸሮቹም ከአንተና ከቤቶችህ፣ ከሹማምንቶችህና ከሕዝብህ ተወግደው በዐባይ ወንዝ ብቻ ይወሰናሉ።”

[12]ሙሴና አሮን ከፈርዖን ዘንድ ከተመለሱ በኋላ፣ በፈርዖን ላይ እግዚአብሔር (ያህዌ) ስላመጣቸው ጓጉንቸሮች ሙሴ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጮኸ። [13]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴ እንደ ለመነው አደረገ፤ ጓጉንቸሮቹም በየቤቱ ውስጥ፣ በየአጥር ግቢውና በየሜዳው ሞቱ። [14]በአንድ ላይ ሰብስበው ከመሯቸው፤ ምድሪቱም ከረፋች። [15]ፈርዖን ችግሩ ጋብ ማለቱን ባየ ጊዜ ግን ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንደ ተናገረው ልቡን በማደንደን ሙሴንና አሮንን አልሰማቸውም።

8፥1 ዘፀ3፥12፤ 4፥23፤5፥1፤9፥1
8፥2 መዝ78፥45፤ 105፥30፤ራእ16፥13
8፥3 ዘፀ10፥6፤ 12፥34
8፥5 ዘፀ4፥2፤7፥9-20፤9፥23፤10፥13፡ 21-22፤14፥27፤4፥17
8፥6 መዝ78፥45፤ 105፥30
8፥7 ዘፀ7፥11፤ ማቴ24፥24
8፥8 ቍ25፡28፤ ዘፀ9፥28፤10፥8፡17፡ 24፤12፥31 ዘኍ21፥7፤1ሳሙ12፥19፤1ነገ13፥6፤ ኤር10፥6፤42፥2፤ 46፥9፤49፥19፤ ሚክ7፥18፤ሐሥ8፥24
8፥9 ዘፀ9፥5
8፥10 ዘፀ9፥14፤ 15፥11፤ዘዳ3፥24፤ 4፥35፤33፥26፤ 2ሳሙ7፥22፤ 1ነገ8፥23፤ 1ዜና17፥20፤2ዜና6፥14፤መዝ71፥19፤86፥8፤89፥6፤113፥5፤ ኢሳ40፥18፤42፥8፤ 46፥9፤ኤር10፥6፤49፥19፤ሚክ7፥18
8፥13 ያዕ5፥16-18
8፥15 ዘፀ7፥14፤ መክ8፥11
8፥16፤ ዘፀ 4፥2
8፥17 መዝ105፥31
8፥18 ዘፀ9፥11፤ ዳን5፥8፤ዘፀ7፥11
8፥19 ዘፀ7፥5፡22፤ 10፥7፤12፥33፤31፥18 ፤1ሳሙ6፥9፤ነህ9፥6፤ መዝ8፥3፤33፥6፤ ሉቃ11፥20
8፥20 ዘፀ3፥18፤ 7፥15፤9፥13
8፥22 ዘፍ45፥10፤ ዘፀ7፥5፤9፥4፡6፡26፡ 29፤10፥23፤11፥7፤ 12፥13፤19፥5፤ዘዳ4፥20፤7፥6፤14፥2፤26፥18፤1ነገ8፥36፤ ኢዮ36፥11፤ መዝ33፥12፤ 135፥4፤ሚል 3፥17
8፥23 ዘፀ9፥4፡6፤ 10፥23፤11፥7፤12፥13፡23፡27
8፥24 መዝ78፥45፤ 105፥31

## የተባይ መቅሠፍት

[16]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ “አሮንን ‘በትርህን ሰንዝረህ የምድርን ትቢያ ምታ’ በለው፤ ከዚያም በግብፅ ምድር ያለው ትቢያ ሁሉ ተናካሽ ትንኝ ይሆናል” አለው። [17]እነርሱም እንዲሁ አደረጉ፣ አሮን በትሩን እንደ ያዘ እጁን ሲዘረጋና የምድሩን ትቢያ ሲመታ፣ በግብፅ ምድር ያለው ትቢያ ሁሉ ተናካሽ ትንኝ ሆነ። ሰውንም ሆነ እንስሳውን ተናካሽ ትንኝ ወረረው። [18]ነገር ግን አስማተኞቹ በድብቅ ጥበባቸው ተናካሽ ትንኞችን ለመፍጠር ሲሞክሩ አልቻሉም። ተናካሽ ትንኞቹም ከሰውና ከእንስሳው ላይ አልወረዱም ነበር። [19]አስማተኞቹም ፈርዖንን፣ “ይህ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ጣት ነው” አሉት፤ ነገር ግን የፈርዖን ልብ ደንድኖ ስለ ነበር፣ ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንደተናገረው አልሰማቸው አለ።

[20]ከዚህ በኋላ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ “በጧት ተነሥተህ ፈርዖን ወደ ውሃ በሚወርድበት ጊዜ ከፊቱ ቀርበህ እንዲህ በለው፤ ‘እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚለው ይህ ነው፤ ያመልኩኝ ዘንድ ሕዝቤን ልቀቅ። [21]ሕዝቤ እንዲሄዱ ባትለቃቸው፣ በአንተና በሹማምንትህ ላይ፣ በሕዝብህና በቤቶችህ ላይ የዝንብ መንጋ እሰዳለሁ። ያረፉበት መሬት እንኳ ሳይቀር፣ የግብፃውያን ቤቶች ሁሉ ዝንብ ብቻ ይሆናሉ።

[22]“ ‘በዚያች ዕለት ግን ሕዝቤ የሚኖርባትን የጌሤምን ምድር የተለየች አደርጋታለሁ፤ እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) በዚህች ምድር እንዳለሁ ታውቅ ዘንድ የዝንብ መንጋ በዚያ አይኖርም። [23]በሕዝቤና በሕዝብህ መካከል ልዩነት አደርጋለሁ፤ ይህ ታምራዊ ምልክት ነገ ይሆናል[†]።’ ”

[24]እግዚአብሔርም (ያህዌ) እንዲሁ አደረገ፤

[†]23 የሰብዓ ሊቃናትና የቩልጌት ትርጕም እንደ ዕብራይስጡ፣ *ዐርነት ነገ ይሆናል* ይላሉ።

8፥2 *አገርህን ሁሉ ጓጉንቸር እመታለሁ፤* እንቍራሪት ሐቄት የተባለች እንስት አምላክ የምትመሰልበት ሲሆን፣ ሴቶች ልጆች በሚወልዱበት ጊዜ የምትረዳቸው ሐቄት ናት ተብሎ ይታሰባል።

8፥13 *እግዚአብሔርም ሙሴን እንዳለው አደረገ፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ አባባል በቍ 31፤ 1ሳሙ 12፥18፤ 1ነገ 18፥42-45፤ አሞ 7፥1-6 ይመ።

8፥16 *ትቢያው ሁሉ ተናካሽ ትንኝ ይሆናል፤* “ትቢያው” የሚለው ቃል ምናልባት የቍጥሩን እጅግ መብዛት ያመለክታል፤ (ዘፍ 13፥16 ይመ)።

8፥19 *የእግዚአብሔር ጣት፤* እግዚአብሔር የታምራት አምላክ መሆኑን እጥር ምጥን ባለ ምሳሌያዊ አነጋገር ይገልጻል (31፥18፤ መዝ 8፥3 ይመ)። ኢየሱስ አጋንንትን ያስወጣው “በእግዚአብሔር ጣት” ነው፤ (ሉቃ 11፥20)። በ9፥3 ላይ “የእግዚአብሔር እጅ” ተብሎ ተጠቅሶአል።

8፥21 *የዝንብ መንጋ እሰድዳለሁ፤* ሰዎችንና እንስሳትን የሚናከስ ዝንብ ነው።

8፥22 *“እለያለሁ”፤* 33፥16 ይመ። እግዚአብሔር በሙሴ ሕዝብና በፈርዖን ሕዝብ መካከል “ልዩነት ያደርጋል”፤ (ቍ 23)፤ በዚህ ላይ በተደረገው መቅሰፍትና በአምስተኛው መቅሠፍት (9፥4፡ 6 ይመ)፣ በሰባተኛው መቅሠፍት (9፥26 ይመ)፣ በዘጠነኛው መቅሠፍት (10፥23 ይመ) እንዲሁም በዐሥረኛው መቅሠፍት (11፥7 ይመ)፤ በፈርዖንና በእርሱ ሕዝብ መካከል ልዩነት ያደርጋል። ይህ የሚያሳየው እግዚአብሔር ግብፃውያንን እየቀጣ ሕዝቡን መጠበቅና መታደግ የሚችል አምላክ መሆኑን ነው። *ጌሤም፤*

አስጨናቂ የዝንብ መንጋ በፈርዖን ቤተ መንግሥትና በሹማምንቶቹ ቤቶች ላይ ወረደ፤ መላው የግብፅ ምድር ከዝንቡ የተነሣ ተበላሽቶ ነበር።

[25]ከዚያም ፈርዖን ሙሴንና አሮንን አስጠርቶ፣ “ሂዱና በዚሁ ምድር ለአምላካችሁ ሠዉ” አላቸው።

[26]ሙሴ ግን እንዲህ አለ፤ “ይህ ትክክል አይሆንም፤ ለአምላካችን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የምናቀርበው መሥዋዕት በግብፃውያን ዘንድ አስጸያፊ ነው፤ ታዲያ በእነርሱ ዐይን አስጸያፊ የሆነውን መሥዋዕት ብናቀርብ አይወግሩንምን? [27]ለአምላካችን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) እርሱ እንዳዘዘን መሥዋዕት ለመሠዋት ወደ ምድረ በዳ የሦስት ቀን መንገድ መሄድ አለብን።

[28]ፈርዖንም፣ “ለአምላካችሁ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በምድረ በዳ መሥዋዕት እንድትሠዉ እፈቅድላችኋለሁ፤ ነገር ግን ርቃችሁ እንዳትሄዱ። ለእኔም ጸልዩልኝ” አላቸው።

[29]ሙሴም እንዲህ አለ፤ “ከአንተ እንደ ተለየሁ ወዲያውኑ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) እጸልያለሁ፤ ነገም ዝንቡ ሁሉ ከፈርዖን፣ ከሹማምንቶቹና ከሕዝቡ ይወገዳል። ብቻ ሕዝቡ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መሥዋዕት እንዲሠዉ ባለመፍቀድ ከዚህ ቀደም ፈረዖን አታሎ እንዳደረገው አሁንም እንዳያደርግ እርግጠኛ ይሁን።”

[30]ከዚያም ሙሴ ከፈርዖን ተለይቶ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጸለየ። [31]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴ የለመነውን አደረገ። የዝንቡም መንጋ ከፈርዖን፣ ከሹማምንቶቹና ከሕዝቡ ተወገደ፤ አንድም ዝንብ እንኳ አልቀረም። [32]በዚህም ጊዜ እንኳን ፈርዖን ልቡን አደነደነ እንጂ፣ ሕዝቡን አለቀቀም።

## የእንስሳት እልቂት

**9** ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ “ወደ ፈርዖን ሂድና እንዲህ በለው፤ ‘የዕብራውያን ስዕባክ (ኤሎሂም) እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚለው ይህ ነው፤ “ያመልኩኝ ዘንድ ሕዝቤን ልቀቅ።” [2]አሁንም እንዳይሄዱ ብታደርግና ብትከለክላቸው፣ [3]የእግዚአብሔር (ያህዌ) እጅ በመስክ ላይ ባሉት እንስሳት፣ በፈረሶችህና በአህዮችህ፣ በግመሎችህና በቀንድ ከብቶችህ፣ በበጎችህና በፍየሎችህ ላይ አስከፊ መቅሠፍት ያመጣብሃል። [4]ነገር ግን እግዚአብሔር (ያህዌ) በእስራኤልና በግብፅ እንስሳት መካከል ልዩነት ያደርጋል፤ ይኸውም የእስራኤል የሆነ ማንኛውም እንስሳ እንዳይሞት ነው።’ ”

[5]እግዚአብሔር (ያህዌ) ጊዜን ወስኖ፣ እንዲህ አለ፤ “በነገው ዕለት እግዚአብሔር (ያህዌ) በምድሪቱ ላይ ይህን ያደርጋል።” [6]በማግሥቱም እግዚአብሔር (ያህዌ) ነገሩን ፈጸመው፤ የግብፃውያን እንስሳት በሙሉ አለቁ፤ ነገር ግን የእስራኤላውያን ከሆኑት እንስሳት አንድም አልሞተም። [7]ፈርዖን ያጣሩ ዘንድ ሰዎች ልኮ ከእስራኤላውያኑ እንስሳት አንድም እንኳን አለመሞቱን ተገነዘበ። ያም ሆኖ ልቡ እንደ ደነደነ ስለ ነበር፣ ሕዝቡን አልለቀቀም።

## የእባጭ መቅሠፍት

[8]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን አላቸው፤ “ከምድጃው እፍኝ ዐመድ ወስዳችሁ፣ ሙሴ በፈርዖን ፊት ወደ ሰማይ ይበትነው። [9]በግብፅ ምድር ሁሉ ትቢያ ይሆናል፤ በምድሪቱ ሁሉ በሚገኙት ሰዎችና እንስሳት ላይ መግል የያዘ እባጭ ይወጣል።”

[10]ስለዚህ ከምድጃው ዐመድ ወስደው በፈርዖን ፊት ቆሙ፤ ሙሴም ወደ ሰማይ በተነው፤ መግል የያዘ እባጭም በሰዎችና በእንስሳት ላይ ወጣ። [11]በእነርሱና በግብፃውያን ሁሉ ላይ እባጭ ወጥቶ ስለ ነበር፣ አስማተኞቹ በሙሴ ፊት መቆም አልቻሉም። [12]እግዚአብሔር (ያህዌ) ግን የፈርዖንን ልብ አደነደነ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ እንደ ተናገረውም፣ ሙሴንና አሮንን መስማት አልፈለገም።

## የበረዶ መቅሠፍት

[13]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ “ማልደህ በማለዳ ተነሣ፤ ከፈርዖን ፊት ቀርበህ እንዲህ በለው፤ ‘የዕ

8፥25 ቍ8፤ ዘፀ9፥27፤10፥16፤ 12፥31
8፥26 ዘፍ43፥32
8፥27 ዘፍ30፥36፤ ዘፀ3፥18
8፥28 ቍ8፤ ኤር37፥3፤ሐሥ8፥24
8፥29 ቍ15፤ ዘፀ9፥30፤10፥11፤ኢሳ26፥10
8፥30 ቍ12፤ዘፀ 9፥33፤10፥18
8፥32 ዘፀ7፥14
9፥1 ዘፀ8፥1
9፥3 ዘፀ7፥4፤ ዘሌ26፥25፤ 1ሳሙ5፥6፤ኢዮ13፥21፤መዝ32፥4፤39፥10፤78፥50፤አሞ4፥10 ሐሥ13፥11
9፥4 ቍ26፤ ዘፀ8፥23
9፥6 ቍ19-21፤ ዘፀ11፥5፤12፥29፤ መዝ78፥48-50
9፥7 ዘፀ7፥14፡ 22፤8፥32
9፥9 ዘሌ13፥18፡ 19፤ዘዳ28፥27፡35፤ 2ነገ20፥7፤ኢዮ2፥7፤ ኢሳ38፥21፤ራእ16፥2
9፥11 ዘፀ8፥18
9፥12 ዘፀ4፥21፤7፥4
9፥13 ዘፀ3፥18

የዘፍ45፥10 ማብ ይመ። እንዲሁም ዘፍ43፥32 እና ማብ ይመ።

8፥31 *እግዚአብሔርም ሙሴ የለመነውን አደረገ፤* የቍ 13 ማብ ይመ።

9፥3 *የእግዚአብሔር እጅ፤* የ8፥19 ማብ ይመ። *በከብቶችህ ... ላይ ... ብርቱ ቸነፈር ይወርዳል፤* ግብፃውያን በርካታ እንስሳትን ያመልኩ ነበር። በወይፈን የሚመሰለው አጲስ፣ በላም የምትመሰለው ሐቶር እና በበግ የሚመሰለው እኑም የእግዚአብሔርን ብርቱ እጅ መቋቋም አልቻሉም፤ እዚህ ላይ የግብፃውያን አማልክት እንደተዋረዱ መመልከት ይቻላል፤ (የቍ 7፥19 ማብ ይመ)።

9፥4 *“ልዩነት ያደርጋል”፤* የ8፥22 ማብ ይመ።

9፥5 *በነገው ዕለት፤* እግዚአብሔርን የሚፈሩ ግብፃውያን ከብቶቻቸውን ወደ ቤቶቻቸው እንዲያሸሹና ከእግዚአብሔር መቅሠፍት እንዲሸሸጉ ቀኙ ለመስጠት ነው፤ (ቍ 20 ይመ)።

9፥6 *የግብፃውያን እንስሳት በሙሉ አለቁ፤* የሞቱት፣ ከየተሠማሩበት ተሰብስበው ወደ ቤት ያልገቡት እንስሳት በሙሉ ናቸው። ወደ ቤት የገቡ እንስሳት አልሞቱም (ቍ 19-21 ይመ)።

9፥8 *ዐመድ ወስዳችሁ ... ወደ ሰማይ ይበትነው፤* የግብፅ ሕዝብና እንስሳት በሙሉ በቍስል እንደሚመቱ የሚያመለክት ምሳሌ ሊሆን ይችላል። *ከምድጃ፤* ምናልባት ጡቦችን ለማድረቅ የሚያገለግል ምድጃና የእስራኤልን ባርነት የሚያመለክት ነው፤ (1፥14፤ 5፥7-19 ይመ)። ይህ ቃል በዘፍ 19፥28 ላይ የሰዶምንና የገሞራን ጥፋት ምፀታዊ በሆነ አገላለጽ ለማመልከት ገብቶአል።

9፥9 *እባጭ፤* ምናልባት እንስሳትን የሚያጠቃው አባ ሰንጋ የተባለ የቆዳ በሽታ ሳይሆን አይቀርም (ቍ 1-7 ይመ)፤ እባጩ እያደር ወደ መግልነት ይቀየራል። *በሰውና በእንስሳት፤* መቅሠፍቱ የግብፅን እንስሳትና ሕዝብ ሁሉ እያስጨነቀ ነው።

9፥11 *አስማተኞቹ ... መቆም አልቻሉም፤* “የግብፅ ቍስል” (ዘዳ 28፥27) ቅልጥምጥምና ጭንን ከፉኛ ያሽመደምዳል (ዘዳ 28፥35 ይመ)።

9፥12 *እግዚአብሔርም የፈርዖንን ልብ አደነደነ፤* የ4፥21 ማብ ይመ።

ብራውያን አምላክ ስግዚስብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚለው ይህ ነው፤ ያመልኩኝ ዘንድ ሕዝ ቤን ልቀቅ፤ [14]አለዚያ በአንተ በሹማምንቶ ችህና በሕዝብህ ላይ የመቅሠፍቴን መዓት ሁሉ አሁን አወርድብሃለሁ፤ ይኸውም በም ድር ሁሉ እንደ እኔ ያለ ማንም እንደሌለ ታውቅ ዘንድ ነው:: [15]አሁን እጄን ዘርግቼ አንተንና ሕዝብህን ከገጸ ምድር ሊያጠ ፉችሁ በሚችል መቅሠፍት በመታኋችሁ ነበር:: [16]ነገር ግን ኀይሌን እንዳሳይህና ስሜም በምድር ዙሪያ ሁሉ እንዲታወቅ ለዚህ አስነሥቼሃለሁ::[a] [17]እስካሁንም በሕ ዝቤ ላይ እንደ ተነሣህ ነው፤ ይሄዱም ዘንድ አትለቃቸውም:: [18]ስለዚህ ነገ በዚህ ጊዜ ከተመሠረተችበት ጊዜ ጀምሮ እስካ ሁን ድረስ በግብፅ ላይ ወርዶ የማያውቅ አስከፊ የበረዶ ማዕበል እልካለሁ:: [19]ከብቶ ችህና በመስክ ላይ ያለህ ማንኛውም ነገር ወደ መጠለያ ይገቡ ዘንድ አሁን ትእዛዝ ስጥ፤ ምክንያቱም በረዶው ወደ መጠለያ ባልገቡትና በመስክ ላይ በቀሩት በማንኛ ውም ሰውና እንስሳት ላይ ወርዶባቸው ስለ ሚሞቱ ነው::

[20]የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ቃል የፈሩት የፈርዖን ሹማምንቶች፣ ባሮቻቸውንና ከብቶ ቻቸውን ለማስገባት ተጣደፉ:: [21]የእግዚአ ብሔርን (ያህዌ) ቃል ችላ ያሉት ግን ባሮቻ ቸውንና ከብቶቻቸውን በመስክ ላይ እንደ ነበሩ ተዉአቸው::

[22]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "በመላይቱ የግብፅ ምድር ባሉት ሰዎች፣ በእንስሳት እንዲሁም በምድሪቱ ላይ በሚበ ቅሉት ነገሮች ሁሉ ላይ በረዶ እንዲወርድ እጅህን ወደ ሰማይ አንሣ" አለው:: [23]ሙሴ በትሩን ወደ ሰማይ ባነሣ ጊዜ እግዚአ ብሔር (ያህዌ) ነጐድጓድና በረዶ አወረደ፤ መብረቅም በምድሪቱ ላይ ሆነ:: እግዚአብ ሔር (ያህዌ) በግብፅ ምድር በረዶ አዘነበ፤ [24]በረዶ ወረደ፤ መብረቅም አብረቀረቀ፤ ግብፅ ሐገር ከሆነችበት ዘመን አንሥቶ በምድሪቱ ሁሉ እንደዚህ ያለ አስከፊ ማዕ በል ሆኖ አያውቅም:: [25]በመላው ግብፅ በረዶ በመስክ ላይ ያለውን ሁሉ፣ ሰዎችንና እንስሳትንም መታ፤ በመስክ ላይ የበቀለ ውን ሁሉ አጠፋ፤ ዛፉን ሁሉ ባዶ አስቀረ:: [26]በረዶ ያልወረደበት ቢኖር እስራኤላውያን የሚኖሩበት የጌሤም ምድር ብቻ ነበር::

[27]ከዚያም ፈርዖን ሙሴንና አሮንን አስጠራ፤ እንዲህም አላቸው፤ 'አሁንስ በድ ያለሁ፤ እግዚአብሔር ' (ያህዌ) ትክክል ነው፤ እኔና ሕዝቤ ግን ስተናል:: [28]መብረቅና በረዶ በዝቶብናልና ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጸልዩልን፤ እንድትሄዱ እለቃችኋለሁ፤ ከዚህ በኋላ በዚህ የመኖር ግዴታ የለባችሁም::

[29]ሙሴም መለሰ፣ "ከከተማዋ በወጣሁ ጊዜ፣ እጆቼን ለጸሎት ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) እዘረጋለሁ፤ አንተም ምድር የእግዚ አብሔር (ያህዌ) እንደ ሆነች ታውቅ ዘንድ መብረቁ ያቆማል፤ ከእንግዲህ በኋላ በረዶ አይኖርም:: [30]ሆኖም አንተና ሹማምንቶችህ አሁንም ቢሆን እግዚአብሔር (ያህዌ) አምላ ክን እንደማትፈሩ ዐውቃለሁ::

[31]ተልባው አብቦ፣ ገብሱም ፍሬ ይዞ ስለነበር፣ ተልባውና ገብሱ ከጥቅም ውጭ ሆኑ:: [32]ስንዴውና አጃው ግን በዚያ ወቅት ባለማፍራቱ አልጠፉም ነበር::

[33]ከዚያም ሙሴ ከፈርዖን ተለይቶ ከከተማው ወጣ:: እጁን ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ዘረጋ፤ ነጐድጓዱና በረዶው ቆመ፤ ዝናቡም በምድሪቱ ላይ መዝነቡን አቆመ:: [34]ፈርዖንም ዝናቡ፣ በረዶውና ነጐድጓዱ መቆሙን ባየ ጊዜ እንደገና በደለ፤ እርሱና ሹማምንቶቹ ልባቸውን አደነደኑ:: [35]ስለዚህ የፈርዖን ልብ ደነደነ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ እንደ ተናገረውም እስራኤላውያን ይሄዱ ዘንድ አልለቀቃቸውም::

## የአንበጣ መንጋ መቅሠፍት

**10** ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "ተመልሰህ ወደ ፈርዖን ሂድ፤ እነዚህን ታምራዊ ምል ክቶች በመካከላቸው ለማድረግ የፈርዖንንና የሹማምንቱን ልብ አደንድኛለሁና፤ [2]ይኸ ውም ግብፃውያንን እንዴት አድርጌ እንደ ቀጣኋቸውና በመካከላቸውም ምልክቶቼን እንዴት እንዳደረግሁ ለልጆቻችሁና ለልጅ ልጆቻችሁ እንድትነግሩና እኔ እግዚአ ብሔር (ያህዌ) መሆኔንም እንድታውቁ ነው::"

[3]ሙሴና አሮን ወደ ፈርዖን ሄደው እንዲህ አሉት፤ "የዕብራውያን ስምላክ እግዚ

9፥14 ዘፀ8፥10፤ 15፥11፤1ሳሙ2፥2፤ 2ሳሙ7፥22፤1ነገ8፥23፤1ዜና17፥20፤ መዝ35፥10፤71፥19፤ 86፥8፤89፥6፤ ኢሳ46፥9፤ኤር10፥6፤ ሚክ7፥18
9፥15 ዘፀ3፥20
9፥16 ዘፀ14፥4:17: 31፤ምሳ16፥4፤ መዝ20፥6፤25፥11፤ 68፥28፤71፥18፤ 106፥8፤109፥21፤ ሮሜ9፥17
9፥18 ቍ23:24፤ ዘፀ10፥6፤ኢሱ10፥11፤ መዝ78፥47-48፤ 105፥32፤148፥8፤ ኢሳ30፥30፤ ሕዝ38፥22፤ ሐጌ2፥17፤
9፥20 ምሳ13፥13
9፥21 ዘፍ19፥14፤ ሕዝ33፥4-5
9፥23 ቍ18፤ ዘፀ20፥18፤ 1ሳሙ7፥10፤12፥17፤ መዝ18፥13፤29፥3፤ 68፥33፤77፥17፤ 104፥7፤ራእ8፥7፤ 16፥21
9፥24 ቍ18
9፥25 መዝ105፥ 32-33፤ሕዝ13፥13
9፥26 ቍ4፤ ኢሳ32፥18-20፤ ዘፀ10፥23፤11፥7፤ 12፥13፤አሞ4፥7
9፥27 ቍ34፤ ዘፀ10፥16፤ዘኍ14፥ 40፤ዘዳ1፥41፤ኢሱ7፥ 11፤መሳ10፥10፤ 1ሳሙ15፥24፤ 24፥17፤26፥21፤ መዝ11፥7፤116፥5፤ 119፥137፤129፥4፤ 145፥17፤ኤር12፥1፤ ሰቆ1፥18
9፥28 ዘፀ8፥8፤ ሐሥ8፥24
9፥29 ቍ33፤ ዘፀ19፥5፤1ነገ8፥22: 38፤ኢዮ11፥13፤ 41፥11፤ምሳ24፥1፤ 50፥12፤መዝ24፥1፤ 50፥12፤77፥2፤88፥9፤ 143፥6፤ ኢሳ1፥15፤ 1ቆሮ10፥26
9፥30 ዘፀ8፥29
9፥31 ዘዳ8፥8፤ ሩት1፥22፤2፥23፤ 2ሳሙ14፥30፤17፥28 ኢሳ28፥25፤ ሕዝ4፥9፤ኢል1፥11
9፥32 ኢሳ28፥25

9፥35 ዘፀ4፥21 10፥1 ዘፀ4፥21፤3፥19፤7፥3፤ኢሱ24፥17፤ነህ9፥10፤ መዝ74፥9፤105፥26-36 10፥2 ዘፀ6፥2፤12፥26-27፤13፥8:14፤ዘዳ 4፥9፤6፥20፤32፥7፤ኢሱ4፥6፤1ሳሙ6፥6፤መዝ44፥1፤71፥18፤78፥4:5፤ ኢል1፥3 10፥3 1ነገ21፥29፤2ነገ22፥19፤2ዜና7፥14፤12፥7፤33፥23፤ 34፥27፤ኢዮ42፥6፤ኢሳ58፥3፤ዳን5፥22፤ያዕ4፥10፤1ጴጥ5፥6

[a]16 ወይም፣ *ለዚህ ምሕረቴን አሳይቼሃለሁ* ተብሎ ሊተረጐም ይችላል::

*9፥16፤* ጳውሎስ የእግዚአብሔርን ሉዓላዊነት ለማስረዳት ፈልጎ ይህንን ክፍል ጠቅሶአል፤ (ሮሜ 9፥17 ይመ)::

9፥18 *አስከፊ የበረዶ ማዕበል እልካለሁ፤* ወቅቱ ገብስና ተልባ የሚያፈራበት በመሆኑ ዝናሙ አንድም ሳይቀር አጠፋው፤ (ቍ 31-32 ይመ)::

*9፥19-21፤* የቍ 6 ማብ ይመ::

9፥27 *አሁንስ በድያለሁ፤* ፈርዖን ለመጀመሪያ ጊዜ ኀጢአተኛ መሆኑንና ኀጢአቱ ያስከተለውን ጥፋት ተገነዘበ::

9፥29 *እጆቼን ... እዘረጋለሁ፤* 1ነገ 8፥22:38:54፤ 2ዜና 6፥12-13:29፤ ዕዝ 9፥5፤መዝ44፥20፤ 88፥9፤ 143፥6፤ ኢሳ 1፥15፤ 1ጢሞ 2፥8 ይመ:: እጅን ወደ ሰማይ ዘርግቶ ወደላይ በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ የተለመደ ወግ መሆኑን የከርሰ ምድር ተመራማሪዎች አረጋግጠዋል::

9፥30 *እግዚአብሔር አምላክን፤* የዘፍ 2፥4 ማብ ይመ::

*9፥31-32፤* የቀ 18 ማብ ይመ::

9፥32 *አጃው፤* የአጃ እህል በጥንት የግብፃውያን መቃብሮች ውስጥ የተገኘ ሲሆን፣ በቆላ አካባቢዎች በሚገባ መብቀል ይች ላል::

10፥2 *ለልጆቻችሁና ለልጅ ልጆቻችሁ፤* የእግዚአብሔር የማዳን ሥራ በየጊዜው እየተወሳ ለልጆቻችን መነገር አለበት፤ (12፥26-27፤ 13፥8:14-15፤ ዘዳ 4፥9፤ መዝ 77፥11-20፤ 78፥4-6:43-53፤ 105፥26-38፤106፥7-12፤114፥1-3፤135፥8-9፤ 136፥10-15 ይመ)::

*አብሔር* (ኤሎሂም ያህዌ) እንዲህ ይላል፤ ‘ራስህን በፊቴ ለማዋረድ እስከ መቼ እምቢ ትላለህ? ሕዝቤ ያመልኩኝ ዘንድ ልቀቃቸው:: [4]እንዳይሄዱ ብትከለክላቸው ነገ በአገርህ ላይ አንበጣዎችን አመጣለሁ:: [5]አንበጣዎቹም ምድሪቱ እስከማትታይ ድረስ ይሸፍኗታል፤ በመስክህ ላይ እያቈጠቈጠ ያለውን ዛፍ ሁሉ ሳይቀር ከበረዶ የተረፈውንም ጥቂቱን ሁሉ ይበሉታል:: [6]የአንተን፣ የሹማምንትህንና የግብፃውያንን ቤቶች ሁሉ ይሞሏቸዋል፤ ይህም አባቶችህም ሆኑ ቅድመ አያቶችህ በዚህች ምድር ከሰፈሩበት ጊዜ ጀምሮ እስካሁን ድረስ ከቶ አይተውት የማያውቁት ነው::’ ” ሙሴም ተመለሰና ከፈርዖን ተለይቶ ሄደ::

[7]የፈርዖንም ሹማምንት፣ “ይህ ሰው እስከ መቼ ወጥመድ ይሆንብናል? አምላካቸውን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዲያመልኩ ሰዎቹን ልቀቃቸውና ይሂዱ:: ግብፅ መጥፋቷን እስካሁን አልተገነዘብህምን? አሉት::

[8]ከዚያም ሙሴና አሮን ወደ ፈርዖን እንዲመጡ ተደረገ፤ “ሂዱ አምላካችሁን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) አምልኩ፤ ነገር ግን መሄድ የሚገባቸው የትኞቹ ናቸው?” አለ::

[9]ሙሴም፣ “*ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) በዓል ልናከብር ስለሆነ ወጣቶቻችንንና ሽማግሌዎቻችንን፣ ወንድና ሴት ልጆቻችንን፣ የበግና የፍየል መንጋዎቻችንን እንዲሁም የቀንድ ከብቶቻችንን ይዘን እንሄዳለን” አለ::

[10]ፈርዖንም እንዲህ አለ፤ “ከሴቶቻችሁና ከልጆቻችሁ ጋር እንድትሄዱ እለቃችኋለሁ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከእናንተ ጋር ይሁን ነገር ግን ተንኰል አስባችኋል::[ሀ] [11]አይሆንም ወንዶቹ ብቻ እንዲሄዱና *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዲያመልኩ አድርጉ፤ የጠየቃችሁት ይህንኑ ነው::” ከዚያም ሙሴና አሮን ከፈርዖን ፊት እንዲወጡ ተደረገ::

[12]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን፣ “የአንበጣ መንጋ ምድሪቱን እንዲወር ከበረዶ የተረፈውን ሁሉና በማሳም ላይ የበቀለውን ሁሉ ጠርጎ እንዲበላ እጅህን በግብፅ አገር ላይ ዘርጋ” አለው::

[13]ስለዚህ ሙሴ በግብፅ አገር ላይ በትሩን ዘረጋ፤ *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) በዚያን ቀንና ሌሊት በሙሉ በምድሪቱ ላይ የምሥራቅ ነፋስ እንዲነፍስ አደረገ፤ በማግሥቱም ነፋሱ አንበጣዎችን አመጣ:: [14]እነርሱም ግብፅን በሙሉ ወረሩ፤ ስፍር ቍጥር የሌላቸው ሆነው የሀገሪቱን ዳር ድንበር ሁሉ አለበሱ:: እንዲህ ያለ የአንበጣ መዓት ከዚህ ቀደም አልነበረም፤ ወደፊትም ደግሞ አይኖርም:: [15]ምድሩ ሁሉ ጠቍሮ እስኪጨልም ድረስ አለበሱት:: ከበረዶ የተረፈውን በመስክ ላይ የበቀለውንና በዛፍ ላይ ያለውን ፍሬ ሁሉ፣ ጠርገው በሉ:: በግብፅ ምድር ሁሉ በዛፍ ላይ ወይም በተክል ላይ አንዳች ቅጠል አልተረፈም ነበር::

[16]ከዚያም ፈርዖን ሙሴንና አሮንን በፍጥነት አስጠርቶ እንዲህ አላቸው፤ “በአምላካችሁ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) በእናንተም ላይ ኀጢአት ሠርቻለሁ፤ [17]እንግዲህ አሁን አንድ ጊዜ ደግሞ ኀጢአቴን ይቅር በሉኝና ይህንን ቀሣፊ መዓት እንዲያስወግድልኝ አምላካችሁን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ለምኑልኝ::”

[18]ሙሴም ከፈርዖን ዘንድ ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጸለየ:: [19]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነፋሱን ወደ ብርቱ የምዕራብ ነፋስ ለወጠው ያም ነፋስ አንበጣዎቹን እየነዳ ወደ ቀይ ባህር[ለ] ከተታቸው፤ በግብፅ ምድር በየትኛውም ቦታ አንድም አንበጣ አልቀረም:: [20]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ግን የፈርዖንን ልብ አደነደነ፤ ፈርዖንም እስራኤላውያን እንዲሄዱ አልፈቀደም::

## የጨለማ መቅሠፍት

[21]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን፣ “በግብፅ ላይ ድቅድቅ ጨለማ እንዲወርድ እጅህን ወደ ሰማይ ዘርጋ” አለው:: [22]ሙሴም እጁን ወደ ሰማይ ዘረጋ፤ በመላው ግብፅ ላይ ለሦስት ቀናት ድቅድቅ ያለ ጨለማ ሆነ:: [23]በነዚያ ሦስት ቀናት ውስጥ አንዱ ሌላውን ማየት ወይም ከነበረበት ቦታ መንቀሳቀስ አይችልም ነበር:: ይሁን እንጂ እስራኤላውያን በሚኖሩበት ስፍራ ሁሉ ብርሃን ነበር::

[24]ከዚያም ፈርዖን ሙሴን አስጠርቶ፣ “ሂዱና *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) አምልኩ፤ ሴቶቻችሁና ልጆቻችሁ ሳይቀሩ አብረዋችሁ ይሂዱ፤ በጎቻችሁ፣ ፍየሎቻችሁና የጋማ ከብቶቻችሁ ብቻ እዚሁ ይቅሩ” አለው::

10፥4 ዘፀ8፥2፤ 9፥2፤ዘዳ28፥38፤ ምሳ30፥27፤ መዝ105፥34፤ ኢዩ1፥4፤ራእ9፥3
10፥5 ቍ15፤ ዘፀ9፥32፤ኢዩ1፥4
10፥6 ዘፀ9፥18፤ ኢዩ2፥9
10፥7 ዘፍ20፥3፤ዘፀ 8፥19፤23፥33፤34፥12 ፤ዘዳ7፥16፤12፥30፤ 20፥18፤ኢሱ23፥13፤ መሳ2፥3፤8፥27፤16፥5 ፤1ሳሙ18፥21፤መዝ 106፥36፤መክ7፥26፤
10፥8 ዘፀ8፥8
10፥9 ዘፀ3፥18
10፥12 ዘፀ7፥19
10፥13 ቍ4:21-22፤ዘፀ4፥17፤8፥ 5: 17፤9፥23፤1 4፥15-16፤26፥27፤ 17፥5፤ዘኍ20፥8፤ 1ነገ18፥37፤መዝ78፥ 46፤105፥34፤አሞ4፥ 9፤ናሆ3፥16
10፥14 ዘዳ28፥38፤ መዝ78፥46፤ኢሳ33፥ 4፤ኢዩ1፥4፤2፥1-11፡ 25፤አሞ4፥9
10፥15 ዘዳ28፥38፤ መዝ105፥34-35፤ ኢዩ1፥4፤አሞ7፥2፤ ሚል3፥11
10፥16 ዘፀ8፥25፤ 9፥27
10፥17ዘፀ8፥8፤ 1ሳሙ15፥25
10፥18 ዘፀ8፥30
10፥20 ዘፀ4፥21
10፥21 ዘዳ28፥29
10፥22 መዝ105፥ 28፤ኢሳ13፥10፤ 45፥7፤50፥3፤ ራእ16፥10
10፥23 ዘፀ8፥22፤ አሞ4፥7
10፥24 ቍ8-10፤ ዘፍ45፥10፤ ዘፀ8፥8

[ሀ]10 ወይም፣ *ተጠንቀቁ! ችግር ተዘጋጅቶላችኋል!* ተብሉ ሊተረጐም ይችላል::
[ለ]19 በዕብራይስጥ፣ *ያም ሱፍ* ይባላል፤ ይኸውም *የደንገል ባሕር* ማለት ነው

10፥4 *አንበጣዎችን አመጣለሁ!* በመጋቢትና በሚያዝያ ወራት የምሥራቅ ነፋስ (ቍ 13 ይመ) ዕድገቱን ያልጨረሰውንና እህልን ምድምድ አድርጎ የሚበላውን የአንበጣ መንጋ ያመጣል:: እንደ አሁኑ ዘመን ሁሉ፣ በጥንት ዘመንም የአንበጣ መንጋ በጣም ይፈራል፤ የአንበጣ መንጋ የእግዚአብሔር ፍርድ ምልክት ተደርጎ ይወሰዳል፤ (ኢዩ1፥4-7፤2፥1-11፤አሞ7፥1-3 ይመ)::

10፥7 *እስከ መቼ ወጥመድ ይሆንብናል?* የፈርዖን ባለሥጣናት ሙሴ በቍ 3 ላይ የተናገረውን ቃል ምፀታዊ በሆነ መንገድ ጠቅሰው የተናገሩት ቃል ነው:: *ግብፅ ጠፋች!* የሰዎች ዕቡይነትና አለመታዘዝ ጥፋትንና ሞትን ያመጣል::

10፥11 *ወንዶቹ ብቻ መሄድ ትችላላችሁ!* በፈርዖን አስተሳሰብ (1) ሴቶችና ልጆች ባሪያ እንዲሆኑ መቅረት አለባቸው፤ እንዲሁም (2) እግዚአብሔርን ማምለክ የሚችሉት ወንዶች ብቻ ናቸው ማለቱ ሳይሆን አይቀርም::

10፥13 *የምሥራቅ ነፋስ!* የቍ 4 ማብ ይመ::

10፥19 *እግዚአብሔርም ... ብርቱ ነፋስ ... አስነሣ!* የፍጥረት ኀይላት ለፈቃዱ ይገዙለታል፤ (14፥21፤ ማቴ 8፥23-27 ይመ)::

10፥21 *ድቅድቅ ጨለማ የግብፅን ምድር ይሸፍናል!* እንደ ሦስተኛውና ስድስተኛው መቅሠፍት ሁሉ ይህ ዘጠነኛው መቅሠፍት በግብፅ ምድር ላይ እንደሚወርድ ለፈርዖን አልተገለጸም:: ይህ ጨለማ በግብፃውያን ዘንድ ታላቅ አምላክ ተደርጎ የሚቈጠረውን የፀሐይ አምላክ “ራን” ክፉኛ የሚያዋርድ ነው::

[25]ሙሴም እንዲህ አለው፤ “ለአምላካችን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) መሥዋዕትና የሚቃጠል መሥዋዕት እንድንሠዋ ፍቀድልን፤ [26]እንስሶቻችን ሁሉ አብረው መሄድ አለባቸው:: አንድ ሰኰና እንኳን አይቀርም:: ከእንስሶቻችን መካከል ለአምላካችን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) አምልኮ የምናቀርባቸው ይኖራሉ፤ ሆኖም እዚያ ከመድረሳችን በፊት *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ለማምለክ የምናቀርባቸው እንስሳት የትኞቹ እንደ ሆኑ አስቀድመን ለይተን ማወቅ አንችልም::”

[27]ነገር ግን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የፈርዖንን ልብ አደነደነ፤ ፈርዖንም ሕዝቡን መልቀቅ አልፈቀደም:: [28]ፈርዖን ሙሴን፣ “ከፊቴ ጥፋ! ስማ! ሁለተኛ እኔ ዘንድ እንዳ ትደርስ! ፊቴን ባየህበት በዚያ ቀን ፈጽመህ እንደምትሞት ዕወቅ” አለው::

[29]ሙሴም፣ “እንዳልከው ይሁን! እኔም ዳግመኛ ከፊትህ አልደርስም” አለው::

**በበኵሮች ላይ የወረደ መቅሠፍት**

**11** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ “በፈርዖንና በግብፅ ላይ አንድ ሌላ መቅሠፍት አወርድባቸዋለሁ፤ ከዚያም በኋላ ፈርዖን ይለቃችኋል፤ ሲለቃችሁም አንዳችሁን ሳያስቀር ያስወጣችኋል:: [2]ለእስራኤል ሕዝብ ለወንዶቹም ሆነ ለሴቶቹ የብርና የወርቅ ዕቃዎች ከየጐረቤቶቻቸው ስጡን ብለው እንዲወስዱ ንገራቸው:: [3]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) እስራኤላውያን በግብፃውያን ዘንድ ሞገስ እንዲያገኙ አደረጋቸው:: ሙሴም በግብፅ ምድር በፈርዖን ሹማምንትና በመላው ሕዝብ ዘንድ እጅግ የተከበረ ሰው ሆነ::

[4]ከዚህ በኋላ ሙሴ እንዲህ አለ፤ “*እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚለው ይህ ነው፤ ‘እኩለ ሌሊት ሲሆን በመላው የግብፅ ምድር ላይ አልፋለሁ:: [5]በዙፋኑ ላይ ከተቀመጠው ከፈርዖን ልጅ አንሥቶ የወፍጮ መጅ ገፊ እስከ ሆነችው እስከ ባሪያይቱ ልጅ ድረስ በግብፅ ምድር በኵር ሆኖ የተወለደ ወንድ ልጅ ሁሉ ይሞታል፤ እንዲሁም የቀንድ ከብቱ በኵር በሙሉ ያልቃል:: [6]በግብፅ ምድር ሁሉ ከዚህ በፊት ያልተሰማ ወደ ፊትም የማይሰማ ታላቅ ዋይታ ይሆናል:: [7]በእስራኤላውያን ዘንድ ግን በሰውም ሆነ በእንስሳት ላይ ውሻ እንኳ አይጮኽባቸውም::’ በዚህም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በግብፃውያንና በእስራኤላውያን መካከል ልዩነት የሚያደርግ መሆኑን ታውቃላችሁ:: [8]ሹማምንትህ በሙሉ ወደ እኔ ይመጣሉ፤ እጅ እየነሡም ‘አንተም ሆንህ የምትመራቸው ሰዎች በሙሉ ውጡልን’ ብለው ይለምኑኛል፤ እኔም ከዚያ በኋላ እሄዳለሁ::” ከዚያም ሙሴ በታላቅ ቍጣ ከፈርዖን ዘንድ ወጣ::

[9]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን “ድንቅ ሥራዎቼ በግብፅ ምድር በብዛት ይታዩ ዘንድ ፈርዖን እናንተን አይሰማችሁም” አለው:: [10]ሙሴና አሮንም እነዚህን ድንቅ ታምራት በፈርዖን ፊት አደረጉ:: ነገር ግን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የፈርዖንን ልብ አደነደነ፤ ፈርዖንም እስራኤላውያን ከአገሩ ለቀው እንዲሄዱ አልፈቀደም::

**የፋሲካ በዓል**

12፥14-20 ተጓ ምብ - ዘሌ 23፥4-8፤ ዘኍ 28፥16-25፤ ዘዳ 16፥1-8

**12** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን በግብፅ እንዲህ አላቸው፤ [2]“ይህ ወር ለእናንተ የወር መጀመሪያ፣ የዓመቱም መጀመሪያ ይሁንላችሁ:: [3]ለመላው የእስራኤል ሕዝብ ይህንን ንገሩ፤ ይህ ወር በገባ በአሥረኛው ቀን እያንዳንዱ ሰው አንዳንድ ጠቦት ለቤተ ሰቡ፣ አንዳንድ ጠቦት ለአባቱ ቤት ያዘጋጅ:: [4]ማንኛውም ቤተ ሰብ ለአንድ ሙሉ ጠቦት ቍጥሩ አነስተኛ ከሆነ፣ በጐረቤት ያሉትን ሰዎች ቍጥር አስቦ ቅርብ ከሆነው ጋር መካፈል ይኖርበታል፤ እያንዳንዱ ሰው በሚበላው መጠንም ምን ያህል ጠቦት እንደሚያስፈልግ መወሰን ይኖርባችኋል:: [5]የምትመርጡት ጠቦት በግ ወይም ፍየል ሊሆን ይችላል፤ ነገር ግን

10፥25 ዘፍ8፥20፤ ዘፀ18፥12
10፥27 ዘፀ4፥21
10፥29 ዘፀ11፥8፤ ዕብ11፥27
11፥1 ዘፀ3፥20፤6፥1
11፥2 ዘፀ3፥21:22
11፥3 ዘፍ39፥21፤ ዘዳ34፥11፤2ሳሙ7፥9 8፥13፤22፥44፤23፥1፤ አስ9፥4፤መዝ89፥27
11፥4 ዘፀ12፥23: 29፤ኢዮ34፥20፤ መዝ 81፥5
11፥5 ዘፀ4፥23፤ ኢሳ47፥2
11፥6 ዘፀ12፥30፤ ምሳ21፥13፤አሞ5፥17
11፥7 ዘፀ8፥22
11፥8 ዘፀ12፥31-33፤ዕብ11፥27
11፥9 ዘፀ3፥20፤7፥4
11፥10 ዘፀ4፥21፤ ሮሜ2፥5
12፥2 ቍ18፤ ዘፀ13፥4፤23፥15፤ 34፥18፤40፥2፤ ዘዳ16፥1
12፥3 ቍ21፤ ማር14፥12፤1ቆሮ5፥7
12፥5 ዘፀ29፥1፤ ዘሌ1፥3፤3፥1፤4፥3፤ 22፥18-21፤ 23፥12፤ ዘኍ6፥14፤15፥8፤ 28፥3፤ዘዳ15፥ 21፤17፥1፤ዕብ9፥14፤ 1ጴጥ1፥19

*10፥28፤ ፈርዖን ለሙሴ ሌላ ዕድል እንደማይሰጠው አስጠነቀቀው::* ***ፊቴን ባየህበት ቀን፤*** በግብፅ ምድር ጨለማ በሆነበት ሰዓት ይህ ንግግር ምፀታዊ ይመስላል::

*11፥2-3፤* 12፥35-36 ይመ::

11፥4 ***ሙሴም እንዲህ አለው፤*** በ10፥29 ላይ የጀመረውን ንግግር እንደቀጠለ ያሳያል::

11፥5 ***በግብፅም አገር ያለ በኵር ሁሉ … ይሞታል፤*** መዝ 78፥51፤ 105፥36፤ 135፥8፤ 136፥10 ይመ:: አንድ አባት ያለው ዕቅድና ሕልም ሁሉ ከበኵር ልጁ ጋር በጥብቅ የተሳሰረ በመሆኑ ይህ ትልቅ ጥፋት ነው፤ አባት ሲሞት ለበኵር ልጁ የሚሰጠው ድርሻ ከሌሎቹ በእጥፍ ይበልጣል፤ (ዘዳ 21፥17 እና ማብ ይመ):: ከዚህ በተጨማሪ በበኵር ልጅ ላይ የሚደርስ ፍርድ በመላው ኅብረተሰብ ላይ የደረሰ ፍርድ ተደርጐ ይቈጠራል:: ***በወፍጮ እግር እስካለችው ባሪያይቱ ድረስ፤*** በዚያን ዘመን የመጨረሻው ዝቅተኛ ሥራ ነው (ኢሳ 47፥2 ይመ)::

11፥7 ***ልዩነት፤*** የ8፥22 ማብ ይመ::

12፥2 ***ይህ ወር… የመጀመሪያው ወር፤*** እስራኤል ሃይማኖታዊ በዓላቷን በሚገባ ማክበር ትችል ዘንድ የተሰጣት የወር መቍጠሪያ ወይም አቡሻኽር ነው፤ (በገጽ 101 ላይ “የዕብራውያን ወር መቍጠሪያ/አቡሻኽር” የሚለውን ገበታ ይመ):: በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ፣ አዲስ ዓመት የሚውልበትና በሥነ ፍጥረት ሕግ መሠረት ደግሞ አዲስ ሕይወት የሚጀምርበት ቀን የሚውለው በተመሳሳይ ጊዜ ነው:: ይህ ወር እስራኤል ሃይማኖታዊ በዓላትን የምታከብርበት አዲስ ዓመት ተደርጐ የተሰጣት የእግዚአብሔር ሕዝብ ልትሆን የቻለችው ከእግዚአብሔር የማዳን ሥራ የተነሣ መሆኑን እንድታስታውስ ነው:: ከነዓናውያን ይህንን ወር አቢብ ብለው ይጠሩታል (13፥4፤ 23፥15፤ 34፥18፤ ዘዳ 16፥1 ይመ)፤ ትርጕሙም “አዲስ እሸት ወይም ቡቃያ” ማለት ነው:: ከጊዜ በኋላ ባቢሎናውያን ይህንን ወር ኒሳን በማለት ሰየሙት፤ (ነህ 2፥1፤ አስ 3፥7 ይመ):: የእስራኤል የግብርና የቀን መቍጠሪያ የሚጀምረው በመፀው ወራት ነው (የ23፥16 ማብ ይመ)፤ ነገሥታት በሚገዙበት ዘመን በአብዛኛው ይጠቀሙ የነበረው በሕዝብ የወር መቍጠሪያ ነበር:: ሁለቱም የቀን መቍጠሪያዎች (ሕዝባዊውና ሃይማኖታዊው) ከምርኮ በኋላም ጐን ለጐን ይሠራባቸው ነበር:: ዛሬ አይሁድ የሚጠቀሙት በመፀው የሚ ጀምረውን የቀን መቍጠሪያ ብቻ ነው::

12፥3 ***ለመላው የእስራኤል ሕዝብ፤*** በጉባኤ የተሰበሰቡትን እስራኤላውያን ነው::

ምንም ነውር የሌለበትና አንድ ዓመት የሞላው ተባዕት መሆን አለበት:: [6]ወሩ በገባ እስከ አሥራ አራተኛው ቀን ድረስ ጠብቋቸው:: በዚያ ምሽት ጀምበር ስትጠልቅ የእስራኤል ሕዝብ ሁሉ ይረ ዱአቸው:: [7]ከዚያም ከደሙ ወስደው የጠ ቦቶቹ ሥጋ የሚበላበትን የእያንዳንዱን ቤት ደጃፍ መቃንና ጉበን ይቀቡ:: [8]ሥጋ ውንም በዚያችው ሌሊት በእሳት ላይ ጠብ ሰው ከመራራ ቅጠልና ካልቦካ ቂጣ ጋር ይብሉት:: [9]ጥሬውን ሥጋ ወይም ቅቅሉን አትብሉ፤ ነገር ግን ጭንቅላቱን፣ እግሮቹ ንና ሆድ ዕቃውን በእሳት ላይ ጠብሳችሁ ብሉት:: [10]ከሥጋው ተርፎ አይደር፤ ያደረ ቢኖር ግን በእሳት ይቃጠል:: [11]ስትበሉም ልብሳችሁን ለብሳችሁ፣ ባጭር ታጥቃችሁ፣ ጫማችሁን አድርጋችሁ በትራችሁን ይዛ ችሁ በጥድፊያ ብሉት፤ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፋሲካ ነው::

[12]"እኔም በዚያች ሌሊት በግብፅ ምድር ላይ አልፋለሁ፤ ከሰውም ከእንስሳም የተወለ ደውን የበኵር ልጅ ሁሉ እገድላለሁ፤ የግ ብፅን አማልክት ሁሉ እፈርድባቸዋለሁ፤ እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነኝ:: [13]ደሙም ያላ ችሁበትን ቤት ለይቶ የሚያሳይ ምልክት ይሆንላችኋል፤ እኔ ደሙን በማይበት ጊዜ እናንተን አልፋለሁ፤ ግብፅን ስቀጣ መቅሠ ፍቱ አይደርስባችሁም::

[14]"ይህን ቀን መታሰቢያ ታደርጉታላ ችሁ፤ በሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ ቋሚ ሥርዐት ሆኖ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) በዓል አድ ርጋችሁ ታከብሩታላችሁ:: [15]ለሰባት ቀናት እርሾ የሌለበትን ቂጣ ብሉ፤ በመጀመሪ ያው ቀን እርሾን ሁሉ ከቤታችሁ አስወ ግዱ፤ በነዚህ ሰባት ቀናት እርሾ ያለበትን ቂጣ የበላ ማንኛውም ሰው ከእስራኤል ይወ ገድ:: [16]በመጀመሪያውና በሰባተኛው ቀን የተቀደሰ ጉባዔ አድርጉ:: በእነዚህ ቀናት ምንም ዐይነት ሥራ አትሥሩ፤ የምትሠሩት ሥራ ቢኖር ለእያንዳንዱ ምግብ ማዘጋጀት ብቻ ይሆናል::

[17]የቂጣን በዓል አክብሩ፤ ሰራዊታችሁን ከግብፅ ምድር ያወጣሁት በዚች ዕለት ነውና:: ይህን ዕለት ለሚቀጥለው ትውልድ ቋሚ ሥርዐት በማድረግ አክብሩት:: [18]ከመ ጀመሪያው ወር ከአሥራ አራተኛው ቀን ምሽት እስከ ሃያ አንደኛው ቀን ምሽት ድረስ እርሾ የሌለበት ያልቦካ ቂጣ ትበላ ላችሁ:: [19]ለሰባት ቀን እርሾ በቤታችሁ አይ ኑር፤ መጻተኛም ሆነ የአገር ተወላጅ እርሾ ያለበትን ቂጣ የበላ ከእስራኤል ማኅበር ይወገድ:: [20]እርሾ ያለበትን ምንም ነገር አትብሉ፤ በምትኖሩበት ስፍራ ሁሉ ያልቦካ ቂጣ ነዉ መብላት ያለባችሁ::

[21]ከዚያም ሙሴ የእስራኤልን ሕዝብ አለቆች በሙሉ አስጠርቶ እንዲህ አላቸው፤ "ቶሎ ሄዳችሁ ለየቤተ ሰቦቻችሁ የሚሆን ጠቦት መርጣችሁ የፋሲካን በግ እረዱ:: [22]ከዚያም ጭብጥ የሂሶጵ ቅጠል በመውሰድ፣ በሳህን ውስጥ ካለው ደም ነክራችሁ

12፥6 ቍ 19፤ ዘፀ16፥12፤ዘሌ23፥5፤ ዘኍ9፥1-3:5:11፤ ዘዳ16፥4:6፤ኢሱ5፥10፤2ዜና30፥2
12፥7 ቍ 13:23፤ ሕዝ9፥6
12፥8 ቍ 10:19-20፤ዘፀ13፥3፤16፥19፤23፥18፤34፥25፤ ዘሌ7፥15፤ዘኍ9፥11:12፤ዘዳ16፥3-4:7፤ 2ዜና35፥13፤ 1ቆሮ5፥8
12፥9 ዘፀ29፥13:17:22፤ዘሌ3፥3
12፥10 ቍ 8፤ ዘፀ13፥7:29፥34፤ ዘሌ22፥30፤ዘዳ16፥4
12፥11 ቍ 13:21:27:33:43፤ዘሌ23፥5፤ ዘኍ9፥2:4፤28፥16፤ ዘዳ16፥1:3፤ ኢሱ5፥10፤ 2ነገ23፥21:23፤ 2ዜና30፥1፤ዕዝ6፥19፤ ኢሳ31፥5፤48፥20፤ 52፥12፤ሕዝ45፥21
12፥12 ቍ 29፤ ዘፀ4፥23፤6፥2፤ 13፥15፤15፥11፤ 18፥11፤ዘኍ33፥4፤ 2ዜና2፥5፤መዝ95፥3፤ 97፥9፤135፥5፤ ኢሳ10፥33፤19፥1፤ 31፥8፤37፥36፤ ኤር 43፥12፤ 44፥8፤አሞ5፥17፤
12፥13 ቍ 11:23፤ዘፀ 8፥23፤ ዕብ11፥28
12፥14 ቍ 17:24፤ዘፀ13፥5:10:9፤ 23፥14፤27፥21፤ 32፥5፤ዘሌ3፥17፤ 10፥9፤16፥29፤ 17፥7፤23፥14፤24፥3፤ዘኍ18፥23 12፥15 ዘፍ17፥14፤ዘፀ13፥6-7፤ 23፥15፤34፥18፤ዘሌ23፥6፤ዘኍ28፥17፤ዘዳ16፥3፤1ቆሮ5፥7 12፥16 ዘኍ29፥35 12፥17 ቍ 41፤ዘፀ6፥6:26፤13፥3፤23፥15፤34፥18፤ዘሌ 3፥17፤19፥36፤ዘዳ16፥16፤2ዜና8፥13፤30፥21፤ዕዝ6፥22፤ማቴ26፥17፤ ሉቃ22፥1፤ሐሥ12፥3፤ 12፥18 ቍ 2 12፥19 ዘፍ17፥14፤ ዘኍ9፥14፤15፥14፤35፥15፤ዘዳ1፥16፤ኢሱ8፥33 12፥20 ዘሌ3፥17፤ ዘፀ13፥6፤ዘኍ35፥29፤ሕዝ6፥6 12፥21 ቍ 11፤ማር14፥12-16 12፥22 ዘሌ14፥4:6፤ ዘኍ19፥18፤መዝ51፥7፤ዕብ11፥28

12፥5 *ነውር የሌለበት ... ከበጎች ወይም ከፍየሎች ውሰድ፤* ዘሌ 22፥18-25 ይመ:: ልክ እንዲሁ ኢየሱስም "ነውርና እድፍ እንደሌለው ... በግ" ነው (2ጴጥ 1፥19)::

12፥6 *ሲመሽ፤* ቃል በቃል ሲተረጉም "በሁለት ምሽት መካከል" ማለት ነው:: ከፈሊጣዊ አነጋገር አንጻር ፍቺው፤ (1) በፀሐይ ማዘቅዘቂያና በፀሓይ መጥለቂያ መካከል ወይም (2) በፀሓይ መጥለቂያና በእኩለ ለሊት መካከል ማለት ነው፤ ይህም የሰንበ ትና ሌሎች ሃይማኖታዊ በዓላት የሚጀምሩት መቼ እንደ ሆነ በትክክል ለመናገር አስቸጋሪ አድርጉታል::

12፥7 *ደም፤* ምትክ ሆኖ የቀረበውን መሥዋዕት የሚያመ ለክት ነው፤ *ሕይወት፤* በሌላ ሕይወት ምትክ ቀረበ (ዘሌ 17፥11 ይመ):: በዚህ ዐይነት እስራኤል በቀረበው መሥዋዕት አማካይነት በግብፅ ላይ ሊወርድ ካለው ፍርድ አመለጠች፤ (ዕብ 9፥22፤ 1ዮሐ 1፥7 ይመ)::

12፥8 *ከመራራ ቅጠል፤* እንዲህ ያሉ መራራ ቅጠሎች በግብፅ ቡብዛት ይገኛሉ። እነዚህን ቅጠሎች መብላት በግብፅ ያሳለፉትን መራራ የባርነት ዘመን ያስታውሳቸዋል፤ (1፥14 ይመ):: *ካልቦካ ቂጣ፤* ከግብፅ ሲወጡ በችኮላ እንደወጡ ያመለክታል፤ (ቍ 1፥39፤ ዘዳ 16፥3 ይመ)::

12፥9 *ራሱን፣ እግሮቹን የሆድ ዕቃውንም ... ጠብሳችሁ ብሉት፤* ዘላን እረኞች ሥጋ ጠብሰው የሚበሉት በዚህ ዐይነት ነው::

12፥11 *ፋሲካ፤* የደሙ ምልክት ያለባቸውን ቤቶች ሳያ ጠፋ "አልፎ እንደሚሄድ" በቍ 13:23:27 ላይ ተገልጾአል::

12፥12 *የግብፅንም አማልክት ሁሉ እፈርድባቸዋለሁ፤* ቀደም ሲል አንዳንዶች ተፈርዶባቸዋል፤ (የ7፥19፤ 8፥1፤ 9፥3፤ 10፥21 ማብ ይመ)፤ አሁን ደግሞ ሁሉም ይፈረድባቸዋል፤ እንዲ ሁም (1) የግብፅ አማልክት፣ በግብፅ ላይ የመጣውን ፍርድ ለማ ስቆም ኀይል እንደሌላቸው በገሃድ ይታያል፤ (2) የግብፅ አማል ክት የሚመሰሉብት እንስሳት ይገደላሉ::

12፥13 *ምልክት፤* በፈርዖንና በሕዝቡ ላይ የወረዱት መቅ ሠፍቶች የፍርድ ምልክት እንደ ነበሩ ሁሉ፣ (8፥23 ይመ)፤ ደሙን ምልክታቸው ያደረጉትን እስራኤላውያንን የእግዚአብሔር "አልፎ መሄድ" የምሕረት ምልክት ነው::

12፥14 *በሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ ታከብሩታላችሁ፤* እስራኤላውያን የፋሲካው በዓል እንዲከበሩ የሚናገሩ ክፍሎች በቅዱ ሳት መጻሕፍት ውስጥ በብዙ ቦታዎች ይገኛሉ፤ (ዘኍ9፥1-5፤ ኢሱ 5፥10፤ 2ነገ23፥21-23፤ 2ዜና30፥1-27፤ 35፥1-19፤ዕዝ6፥19-22፤ ሉቃ2፥41-43፤ዮሐ2፥13:23፤ 6፥4፤ 11፥55-12፥1 ይመ):: ሃይማ ኖት አጥባቂ አይሁዳውያን ዛሬም ይህንን ሥርዐት ያከብራሉ::

12፥15 *ሁሉ ከቤታችሁ አስወግዱ፤* ከጊዜ በኋላ እርሾ እንደ "ግብዝነት" (ሉቃ12፥1) ወይም እንደ "ዐመፅና ክፋት" (1ቆሮ 5፥8) ላሉ ኀጢአቶች ምሳሌ ሆኖአል:: በአሁኑ ጊዜ ሃይማኖት አጥባቂ አይሁዳውያን የፋሲካን በዓል ከማክበራቸው በፊት፣ በቤቶቻቸው ውስጥ እርሾ ያለበት ፍርፋሪ እንዳይገኝ ቤቶቻቸውን በሚገባ ይፈትሻሉ/ያጸዳሉ፤ (ቍ 19 ይመ):: *ከእስራኤል ተለይቶ ይጥፋ፤* ከቃል ኪዳኑ ሕዝብ መካከል ተለይቶ ይገደል፤ (31፥14፤ ዘሌ 20፥2-3) ወይም ከምድረ ገጽ ይጥፋ ማለት ነው:: እንዲሁም ዘፍ 17፥14 እና ማብ ይመ::

12፥17 *የቂጣ በዓል፤* ይህ በዓል የሚጀመረው የፋሲካውን ምግብ በመብላት ሲሆን፣ በዓሉ ለሰባት ቀን ይቀጥላል፤ (ቍ 18-19 ይመ፤ እንዲሁም ማር 14፥12 ይመ)::

12፥21 *የፋሲካን ... በግ፤* ኢየሱስ "የፋሲካችን በግ" (1ቆሮ 5፥7) በመሆኑ፣ "አንድ ጊዜ ፈጽሞ" ራሱን ለእኛ ኀጢአት መሥ ዋዕት አድርጎ አቀረበ፤ (ዕብ 7፥27)::

12፥22 *ሂሶጵ፤* እዚህ ላይ ምናልባት መልካም መዐዛ ያለ ውን ተክል ያመለክታል፤ (ዮሐ 19፥29 ይመ)፤ ይህ ተክል ነጫጭ አበቦች አሉት:: እንደ ጸጉር ባሉ ነገሮች የተሸፈነው የተክሉ ቅጠ ልና ቅርንጫፍ ብዙ ፈሳሽ ወይም ውሃ ስለሚይዝ የመንጻት ሥርዐት በሚደረግበት ጊዜ ለመርጫ የሚያገለግል ጥሩ ተክል

## የዕብራውያን የቀን አቈጣጠር

| የወራት ቍጥር | | የዕብራውያን ስያሜ/አጠራር | ዘመናዊው አቈጣጠር | የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል | የግብርና ወቅት | በዓላት |
|---|---|---|---|---|---|---|
| 1 | 7 | አቢብ፣ ኒሳን | ሚያዝያ | ዘፀ 12÷2፤ 13÷4፤ 23÷15፡34÷18፤ዘዳ 16÷1፤ ነህ 2÷1 ኢሳ3÷7 | የፀደይ ዝናብ፣ የገብስ አዝመራ መሰብሰቢያ | ፋሲካ፣ ያለ እርሾ የተጋገረ ቂጣ በዓል |
| 2 | 8 | ዚፍ (ኢያር)* | ግንቦት | 1ነገ 6÷1፡37 | የገብስ አዝመራ መሰብሰቢያ፣ የበጋ ወቅት ጅማሬ | - |
| 3 | 9 | ሲዋን | ሰኔ | አስ 8÷9 | የስንዴ አዝመራ መሰብሰቢያ | በዓለ አምሳ (ጰንጠቆስጤ) |
| 4 | 10 | (ታሙዝ)* | ሐምሌ | ሕዝ 8÷14 | የወይን ተክል | - |
| 5 | 11 | (አብ)* | ነሐሴ | | የወይን፣ የወይራና የበለስ ፍሬ መብሰቢያ ጊዜ | - |
| 6 | 12 | ኤሉል | መስከረም | ነህ 6÷15 | የወይን፣የወይራ የበለስ ፍሬ መጭመቂያ ጊዜ | - |
| 7 | 1 | ኤታኒም | ጥቅምት | 1ነገ 8÷2 | የበልግ ዝናብ ወቅት፣ መሬት ማለስለሻ ጊዜ | የመለከት፣ የማስተሰርያ፣ የዳስ በዓል |
| 8 | 2 | ቡል | ኅዳር | 1ነገ 6÷38 | ስንዴና ገብስ የሚዘራበት ወቅት | - |
| 9 | 3 | ካሴሉ | ታኅሣሥ | ነህ 1÷1፤ ዘካ 7÷1 | የክረምት ዝናብ ጅማሬ በአንዳንድ ቦታዎች በረዶ የቀላቀለ) | - |
| 10 | 4 | ጤቤት | ጥር | አስ 2÷16 | - | - |
| 11 | 5 | ሳባጥ | የካቲት | ዘካ 1÷7 | - | - |
| 12 | 6 | አዳር | መጋቢት | ዕዝ 6÷15፤ኢሳ 3÷7፡ 13፤ 8÷12፤ 9÷1፡ 15፡17፡19፡21 | የለውዝ ተክል ማበብ፣ የብርቱካን ፍሬ ለቀማ | ፑሪም |

**(አዳር ሴናይ)* ሁለተኛው አዳር** በየሦስት ዓመቱ የሚጨመር ወር ሲሆን ጨረቃማኅ ከጣይዓመት ጋር እንዲስተካከል የሚጨመር ነው።

*በቅንፍ ውስጥ ያሉ ስያሜዎች በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ አይገኙም።

የየቤቶቻችሁን ጉበንና ግራ ቀኝ መቃኑን ቀቡ። ከእናንተ አንድም ሰው እስኪነጋ ድረስ ከቤቱ አይውጣ። [23]እግዚአብሔር (ያህዌ) ግብፃውያንን ለመቅሠፍ በምድሪቱ ላይ በሚያልፍበት ጊዜ በጉበኑና በመቃኑ ላይ ያለውን ደም ሲያይ ያንን ደጃፍ አልፎ ይሄዳል፤ ቀሣፊውም ወደ ቤታችሁ ገብቶ እንዳይገድላችሁ ይከለክለዋል።

[24]"እናንተም ሆነ ልጆቻችሁ ይህን መመሪያ ቋሚ ሥርዐት አድርጋችሁ ትታዘዛላችሁ። [25]እግዚአብሔር (ያህዌ) እሰጣችኋለሁ ብሎ በገባው ቃል መሠረት ወደ ምድሪቱ ስትገቡ ይህን ሥርዐት ጠብቁ። [26]ልጆቻችሁ ስለ ስርዐቱ ምንነት ሲጠይቋችሁ፣ [27]'ግብፃውያንን በቀሠፈ ጊዜ፣ በግብፅ ምድር የእስራኤላውያንን ቤት አልፎ በመሄድ ቤታችንን ሳተረፈ፣ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የፋሲካ መሥዋዕት ነው' ብላችሁ ንገሯቸው።" ከዚያም ሕዝቡ አጐንበሱ፤ ሰገዱም። [28]እስራኤላውያንም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዳዘዛቸው አደረጉ።

[29]እኩለ ሌሊት ላይ እግዚአብሔር (ያህዌ) በግብፅ ምድር በዙፋን ላይ ከተቀመጠው ከፈርዖን የበኵር ልጅ ጀምሮ በጨለማ እስር ቤት ውስጥ እስካለው እስረኛ የበኵር ልጅ ድረስ ያለውንና የእንስሳቱን በኵሮች ሁሉ ቀሠፋቸው። [30]ፈርዖን፣ ሹማምንቱና የግብፅ ሕዝብ በሙሉ ሌሊቱን ከመኝታቸው ተነሡ፤ እነሆ በመላይቱ ግብፅ ለቅሶና ዋይታ ነበር፤ ሰው ያልሞተበት አንድም ቤት አልነበረምና።

## ከግብፅ መውጣት

[31]ፈርዖን ሙሴንና አሮንን ሌሊቱን አስጠርቶ እንዲህ አላቸው፤ "ተነሡ እናንተና እስራኤላውያን ከሕዝቤ መካከል ውጡ! ሂዱ፤ በጠየቃችሁት መሠረት እግዚአብሔርን (ያህዌ) አምልኩ፤ [32]እንዳላችሁት የበግና የፍየል መንጋችሁን፣ የቀንድና የጋማ ከብቶቻችሁን ይዛችሁ ሂዱ፤ እኔንም ባርኩኝ።"

[33]ግብፃውያን አገራቸውን በአስቸኳይ ለቀው እንዲወጡላቸው እስራኤላውያንን አጣደፏቸው። "አለበለዚያማ ሁላችንም ማለቃችን ነው" አሉ። [34]ስለዚህ ሕዝቡ ያልቦካ ውን ሊጥ በየቡሆ ዕቃው አድርገው በጨርቅ ጠቅልለው በትከሻቸው ተሸከሙ። [35]እስራኤላውያን ሙሴ እንዳዘዛቸው የብርና የወርቅ ዕቃዎች እንደዚሁም ልብስ እንዲሰጧቸው ግብፃውያኑን ጠየቋቸው። [36]እግዚአብሔር (ያህዌ) በግብፃውያን ፊት ለእስራኤላውያን ሞገስ ስለሰጣቸው፣ የጠየቋቸውን ሁሉ ሰጧቸው፤ ስለዚህ የግብፃውያንን ንብረት በዝብዘው ወሰዱ።

[37]እስራኤላውያን ከራምሴ ተነሥተው ወደ ሱኮት ሄዱ፤ ከሴቶቹና ከልጆቹ ሌላ፣ ስድስት መቶ ሺህ እግረኛ ወንዶች ነበሩ። [38]ከእነርሱም ጋር ቍጥሩ የበዛ ሌላ ድብልቅ ሕዝብ አብሮአቸው ወጣ፤ እንዲሁም አያሌ የበግ፣ የፍየል፣ የጋማና የቀንድ ከብት መንጋ ይዘው ወጡ። [39]ከግብፅ ይዘው ከወጡት ሊጥ ያልቦካ ቂጣ ጋገሩ፤ ሊጡ አልቦካም ነበር፤ ምክንያቱም ከግብፅ በጥድፊያ እንዲወጡ ስለተደረጉ፣ ለራሳቸው ምግብ ለማዘጋጀት ጊዜ አልነበራቸውም።

[40]እንግዲህ እስራኤላውያን በግብፅ* የኖሩበት ዘመን አራት መቶ ሠላሳ ዓመት ነበር። [41]ልክ አራት መቶ ሠላሳው ዓመት በተፈጸመ ዕለት የእግዚአብሔር (ያህዌ) ሰራዊት ሁሉ ግብፅን ለቆ ወጣ።

[42]እግዚአብሔር (ያህዌ) በዚያች ሌሊት እነርሱን ከግብፅ ለማውጣት ዘብ የቆመበት በመሆኑ፣ ለሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ እግዚአብሔርን (ያህዌ) ያከብሩ ዘንድ፣ በዚያች ሌሊት እስራኤላውያን ሁሉ ዘብ መቆም ይኖርባቸዋል።

## የፋሲካ በዓል እንዴት መከበር እንዳለበት

[43]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ "የፋሲካ በዓል አከባበር ሥርዐት እንዲህ ነው፤ ባዕድ የሆነ ሰው ከፋሲካው ምግብ አይብላ፤ [44]በገንዘብ የገዛኸው ማንኛውም ባሪያ ከገረዝኸው በኋላ መብላት ይችላል [45]ነገር ግን ለጊዜው የተቀመጠ እንግዳና ቅጥር ሠራተኛ መብላት የለበትም።

[46]"ምግቡ በአንድ ቤት ውስጥ መበላት አለበት፤ ምንም ሥጋ ከቤት እንዳይወጣ፤ ምንም አጥንት እንዳትሰብሩ። [47]የእስራኤል

12፥23 ቍ7:13፤ ዘፍ16፥7፤ኢሳ19፥22፤ 37፥36፤ኤር6፥26፤ 48፥8፤1ቆሮ10፥10፤ 11፥28፤ራእ7፥3
12፥24 ቍ14
12፥25 ዘፍ15፥14፤ ዘፀ3፥17
12፥26 ዘፀ10፥2
12፥27 ቍ11፤ዘፍ 24፥26፤ዘፀ8፥23
12፥28 ቍ50
12፥29 ዘፍ19፥13፤ ዘፀ4፥23፤9፥6፤11፥4፤
12፥30 ዘፀ11፥6
12፥31 ዘፀ8፥8
12፥32 ዘፍ27፥34፤ ዘፀ10፥9:26
12፥33 ቍ11፤ ዘፍ20፥3፤ ዘፀ6፥1፤8፥19፤ 1ሳሙ6፥6
12፥34 ዘፀ8፥3
12፥35 ዘፍ24፥53፤ ዘፀ3፥22፤
12፥36 ዘፍ39፥21፤ ዘፀ3፥22
12፥37 ዘፍ12፥2፤ 47፥11፤ዘፀ13፥20፤ 38፥26፤ዘኍ1፥46፤ 2፥32፤11፥13:21፥26 ፤51፤33፥3-5
12፥38 ዘኍ11፥4፤ ኢሱ8፥35
12፥39 ዘፀ3፥20፤ 11፥1
12፥40 ዘፍ15፥13፤ ሐሥ7፥6፤ገላ3፥17
12፥41 ዘፀ3፥10፤ 6፥26
12፥42 ዘፀ13፥10፤ ዘሌ3፥17፤ዘኍ9፥3፤ ዘዳ16፥1:6
12፥43 ቍ11:48፤ ዘኍ9፥14፤15፥14፤ 2ዜና6፥32-33፤ ኢሳ14፥1፤56፥3:6፤ 60፥10
12፥44 ዘፍ17፥12-13
12፥45 ዘሌ22፥10
12፥46 ዘኍ9፥12፤ መዝ22፥14፤34፥20፤ 51፥8፤ምሳ17፥22፤ ዮሐ19፥36

*40 ማሶሬቲክ ቅጂ፣ አራተ ሳምራውያንና የሰብዓ ሊቃናት ትርጉም *በግብፅና በከነዓን* ይላሉ

ነው፤ (14፥4:6:49:51-52፤ ዘኍ 19፥6:18፤ ዕብ 9፥19 ይመ፤ እንዲሁም መዝ 51፥7 ይመ)። *ደም ነክራችሁ፤* በአሁኑ ጊዜ እስራኤላውያን የፋሲካን በዓል ሲያከብሩ በግብፅ ያሳለፉትን የሥቃይ ዘመን ለማስታወስ ሲሉ በጨዋማ ውሃ ውስጥ ቅጠል ነክረው ይበላሉ።

12፥23 *አልፎ ይሄዳል፤* የቍ 11 ማብ ይመ። *አጥፊውም፤* በመዝ 78፥49 ላይ ግብፃውያንን ለማጥፋት የተላከው የእግዚአብሔር ቍጣ "የሞት መልእክተኛ" ተብሎ ተጠቅሶአል። እግዚአብሔር አጥፊ መቅሠፍቶችን ሲልክ መላእክትን ይጠቀማል፤ (2ሳሙ 24፥16-16፤ 2ነገ 19፥35 ይመ፤ እንዲሁም 1ቆሮ 10፥10 ይመ፤ ይህ ጥቅስ የተወሰደው ከዘኍ 16፥41-49 ላይ ነው)።

12፥26 *ልጆቻችሁ ስለ ሥርዐቱ ምንነት ሲጠይቋችሁ፤* 13፥14 ይመ። የፋሲካ በዓል የእስራኤልን መዋጀት ለማስታወስ በየጊዜው መከበር አለበት፤ ምክንያቱም እስራኤል ከግብፅ ባርነት ተዋጅታ የእግዚአብሔር ነጻ ሕዝብ ሆናለች።

12፥27 *የፋሲካ መሥዋዕት፤* የቍ 21 ማብ ይመ። *አልፎ፤* የቍ 11 ማብ ይመ።

12፥29 *በጕድጓድ ውስጥ እስከተጣለው እስረኛ፤* የመጨረሻ ዝቅተኛ መጣያ ስፍራ ነው፤ (የ11፥5 ማብ ይመ)።

12፥31 *ፈርዖንም ሙሴን ... አስጠርቶ፤* ምንም እንኳ ፈርዖን ሙሴን ዳግመኛ ላለማየት ቢምልም፣ (10፥28 እና ማብ ይመ)፤ አሁን ሙሴን (እና አሮንን) ወደ እርሱ እንዲገቡ አስጠራቸው።

*12፥35-36፤* 3፥21-22፤ 11፥2-3 ይመ።

12፥37 *ከራምሴ ተነሥተው ... ጕዞ ጀመሩ፤* 1፥11 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 47፥11 ማብ ይመ። እስራኤላውያን ጕዞ የጀመሩት "ከፋሲካ በኋላ በማግሥቱ" ነው (ዘኍ 33፥3)። *ሱኮት፤* ምናልባት በአሁኑ ጊዜ ቴል ማስኩታ ሳትሆን አትቀርም።

12፥38 *ሌላ ድብልቅ ሕዝብ፤* ምናልባት በ9፥20 ላይ እንደ ተጠቀሰው ግብፃውያንንም ይጨምራል።

12፥41 *አራት መቶ ሠላሳ ዓመት፤* የሐሥ 7፥6 ማብ ይመ።

12፥46 *ዐጥንቶቹን አትስበሩ፤* ዘኍ 9፥12፤ መዝ 34፥20

ሕዝብ ሁሉ በዓሉን ማክበር ይኖርበታል። [48]"በመካከላችሁ የሚኖር መጻተኛ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) የፋሲካ በዓል ማክበር ቢፈልግ፣ በቤተ ሰቡ ያሉት ወንዶች ሁሉ መገረዝ አለባቸው፤ ከዚያም እንደ ተወላጅ ተቈጥሮ የሥርዐቱ ተካፋይ ይሁን። ያልተገረዘ ወንድ ግን የፋሲካን ምግብ አይብላ። [49]ይህም ሕግ በዜጋውም ሆነ በመካከላችሁ በሚኖሩት መጻተኞች ላይ እኩል ተፈጻሚነት ይኖረዋል።"

[50]እስራኤላውያን በሙሉ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን ያዘዘውን ሁሉ ፈጸሙ። [51]በዚያችው ዕለት እግዚአብሔር (ያህዌ) እስራኤላውያንን በየሰራዊታቸው አድርጎ ከግብፅ ምድር አወጣቸው።

## በኵር ሁሉ ለእግዚአብሔር መቀደሱ

**13** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ [2]"መጀመሪያ የተወለደውን ወንድ ሁሉ ለእኔ ቀድስልኝ፤ ከእስራኤላውያን መካከል የእናቱ የበኵር ልጅ የሆነው ማሕፀን ከፋች ሰውም ሆነ እንስሳ የእኔ ነው።"

[3]ከዚያም ሙሴ ሕዝቡን እንዲህ አለ፤ "ከባርነት ምድር ከግብፅ የወጣችሁባትን ይህችን ዕለት አስታውሱ፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር (ያህዌ) በኀያል ክንዱ አውጥቶአችኋል። እርሾ ያለበትን ማንኛውንም ነገር አትብሉ። [4]እነሆ በዚች ዕለት በአቢብ ወር ወጥታችኋል። [5]እግዚአብሔር (ያህዌ) ለእናንተ ለመስጠት ሲል ቀድሞ ለአባቶቻችሁ ወደ ማለላቸው ማርና ወተት ወደምታፈሰው ወደ ከነዓናውያን፣ ኬጢያውያን፣ አሞራውያን፣ ኤዊያውያን፣ ኢያቡሳውያን ምድር በምትገቡበት ጊዜ ይህን በዓል በዚህ ወር ታከብራላችሁ። [6]ለሰባት ቀን ያለ እርሾ የተጋገረ ቂጣ ትበላላችሁ። በሰባተኛውም ቀን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በዓል ታደርጋላችሁ። [7]በእነዚህም ሰባት ቀናት ያልቦካ ቂጣ ትበላላችሁ፤ በእናንተ ዘንድ እርሾ ያለበት ነገር ፈጽሞ አይገኝ፤ በምድራችሁም አዋሳኝ በየትኛውም ቦታ እርሾ ፈጽሞ አይኑር። [8]በዚያችም ዕለት፣ 'እኔ ይህን የማደርገው ከግብፅ ምድር በወጣሁበት ጊዜ እግዚአብሔር (ያህዌ) ስላደረገልኝ ነገር ነው' ብለህ ለልጅህ ንገረው። [9]የእግዚአብሔር (ያህዌ) ሕግ በከንፈራችሁ ላይ እንዲሆን ይህ በዓል ለእናንተ በእጃችሁ ላይ እንደታሰረ ምልክት፣ በእግራችሁ ላይ እንደሚገኝ መታሰቢያ ይሆንላችኋል። እግዚአብሔር (ያህዌ) በኀያል ክንዱ ከግብፅ አውጥቶአችኋልና። [10]ይህን ሥርዐት በተወሰነው ጊዜ በየዓመቱ ጠብቁት።

[11]"እግዚአብሔር (ያህዌ) ለእናንተና ለቀደሙት አባቶቻችሁ በመሐላ በሰጠው ተስፋ መሠረት ወደ ከነዓናውያን አገር በሚያስገባችሁና ምድሪቱንም ለእናንተ በሚሰጣችሁ ጊዜ፣ [12]የእናቱን ማሕፀን የሚከፍተውን ሁሉ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ትሰጣላችሁ፤ እንደዚሁም እንስሶቻችሁ በመጀመሪያ የወለዷቸው ወንዶች ሁሉ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ይሆናሉ። [13]ከአህያ በመጀመሪያ የተወለደውን ውርንጫ ግን በጠቦት ትዋጁታላችሁ፤ አህያውን ካልዋጃችሁት ግን አንገቱን ስበሩት። ከወንድ ልጆቻችሁ መካከል በኵር የሆኑትን ሁሉ ዋጁ።

[14]"በሚመጡት ዘመናት ልጅህ፣ 'ይህ ምን ማለት ነው?' ብሎ ቢጠይቅህ እንዲህ በለው፤ 'ከባርነት ምድር ከግብፅ እግዚአብሔር (ያህዌ) በኀያል ክንዱ አወጣን፤ [15]ፈርዖን እኛን አለቅም ብሎ ልቡን ባደነደነ ጊዜ ከሰው ጀምሮ እስከ እንስሳ ድረስ በኵር ሆኖ በግብፅ የተወለደውን ሁሉ እግዚአብሔር (ያህዌ) ገደለው። እንግዲህ በመጀመሪያ የእናቱን ማሕፀን የከፈተውን ወንድ ሁሉ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የምሠዋውና የልጆቼ በኵር ሆኖ የተወለደውን ወንድ ልጅ ሁሉ የምዋጀው በዚህ ምክንያት ነው። [16]እግዚአብሔር (ያህዌ) በኀያል ክንዱ እኛን ከግብፅ ያወጣን ስለሆነ ይህ ሥርዐት በእጅህም ሆነ በግንባርህ ላይ እንደ ምልክት ይሆናል።"

## ቀይ ባሕርን መሻገር

[17]ፈርዖን ሕዝቡን በለቀቀ ጊዜ አቋራጭ

12፥48 ቍ49፤ ዘሌ19፥18:34፤ 24፥22፤ዘኍ9፥14፤ 10፥32፤ሕዝ44፥7
12፥49 ዘሌ24፥22፤ ዘኍ15፥15-16:29፤ ዘዳ1፥16
12፥50 ቍ28
12፥51 ዘፀ3፥10፤ 6፥6:26
13፥2 ቍ12: 13:15፤ዘፀ22፥29፤ 34፥20፤ዘሌ27፥26፤ ዘኍ3፥13፤8፥17፤ 18፥15፤ዘዳ15፥19፤ ነህ10፥36፤ሉቃ2፥23
13፥3 ቍ14፤ዘፀ 3፥20፤7፥4፤12፥8፤ ዘሌ26፥13፤ዘኍ1፥1፤ 9፥1፤22፥5፤26፥4፤ዘዳ 4፥45፤5፥6፤መዝ81፥ 10፤114፥1
13፥4 ዘፀ12፥2
13፥5 ቍ11፤ ዘፀ3፥8፤12፥25-26
13፥6 ዘፀ12፥15-20
13፥8 ዘፀ10፥2፤ መዝ78፥5-6
13፥9 ቍ16፤ ዘፀ3፥20፤ዘዳ6፥8፤ 11፥18፤ምሳ3፥3፤ ኢሳ44፥5፤ማቴ23፥5
13፥10 ዘፀ12፥14፤ መዝ75፥2፤102፥13
13፥11 ቍ5፤ ዘፍ12፥7፤17፥19፤ 22፥16፤ዘዳ1፥8፤ መዝ105፥42-45
13፥12 ዘፍ4፥4፤ ዘሌ27፥26፤ ዘኍ3፥13፤18፥15: 17፤ሉቃ2፥23
13፥13 ቍ15፤ ዘሌ27፥11፤ ዘፀ34፥20፤ኢሳ66፥3፤ ዘኍ3፥46-47፤18፥15
13፥14 ዘፀ10፥2፤ 20፥2፤ዘዳ7፥8፤28፥68
13፥15 ቍ2
13፥16 ቍ9
13፥17 ዘፀ14፥11፤ ዘኍ14፥1-4፤ዘዳ 17፥16፤ሆሴ11፥5

ይመ፤ በዮሐ 19፥36 ላይ ከኢየሱስ ጋር ተያይዞ ተጠቅሶአል።

12፥48 *ያልተገረዘ ማንም ሰው አይብላ፤* የፋሲካን በግ መብላት የሚችሉት በኪዳኑ መሠረት ራሳቸውን ለእግዚአብሔር የሰጡ ብቻ ናቸው፤ ነገሩ ትርጕም የሚሰጠውም ለእነርሱ ብቻ ነው፤ (ዘፍ 17፥9-14 ይመ)። የጌታን እራት መካፈል ያለባቸው እነማን እንደሆኑ በ1ቆሮ 11፥28 ላይ ይመ።

13፥2 *በመጀመሪያ የተወለደውን ሁሉ ለእኔ ቀድስው፤* እግዚአብሔር እስራኤልን እንደ በኵር ልጁ አድርጎ ወስዶአታል፤ (4፥22 ይመ)፤ እንዲሁም የሰውንም ሆነ የእንስሳትን ተባዕት ሁሉ ከግብፅ ባርነት ነጻ አውጥቶአል፤ ከመቅሠፍቶቹም ታድጎአል (12፥12-13 ይመ)። ስለዚህ በእስራኤል ያለ ማንኛውም በኵር የእርሱ ነው። የማርያም የበኵር ልጅ የሆነው ኢየሱስ (ሉቃ 2፥7 ይመ)፤ ለእግዚአብሔር የተሰጠው በዚህ ሕግ መሠረት ነው፤ (ሉቃ 2፥22-23 ይመ)።

*13፥5፤* የ3፥8 ማብ ይመ።

13፥9 *በእጃችሁ ላይ እንደታሰረ ምልክት በእግራችሁ ላይ እንደሚገኝ መታሰቢያ፤* ምሳሌያዊ አነጋገር ነው፤ (ቍ16፤ዘዳ 6፥8፤ 11፥18 ይመ፤ እንዲሁም ምሳ 3፥3፤ 6፥21 ፤ 7፥3፤ መሓ 8፥6 ይመ)። ይህን ንባብ በቀጥታ (እንደዚሁ እንዳለ) የተረጐሙ አይሁዳውያን በቍ 1-10፡11-16፤ ዘዳ 6፥4-9 እና በዘዳ 11፥13-21 የሚገኙትን ቃላት በብራና ላይ አጽፈው፣ በሁለት ትናንሽ ማኅደሮች ውስጥ ያስቀምጡና ጠዋት ጠዋት ጸሎታቸውን ከማድረጋቸው በፊት፣ አንደኛውን ማኅደር በግንባራቸው ላይ ሁለተኛውን ማኅደር ደግሞ በግራ እጃቸው ላይ ያስሩታል። እነዚህ ማኅደሮች "አሸንክታብ" ተብለው ይጠራሉ (ማቴ 23፥5)። አይሁዳውያን እንዲህ ያለውን ሥርዐት ማድረግ የጀመሩት ከባቢሎን ምርኮ ከተመለሱ በኋላ ነው።

13፥13 *ትዋጁታላችሁ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ዋጋ ከፍላችሁ ነጻ ታወጡታላችሁ" ማለት ነው። *የአህያውን በኵር፤* የጋማ ከብቶች የኢኮኖሚ መሠረት በመሆናቸው እነርሱም የተዋጁት በበግ ነው። *በኵር የሆኑትን ሁሉ፤* ሰዎች ለእግዚአብሔር መሰጠት ወይም መለየት ያለባቸው በሕይወት እያሉ እንጂ ከሞቱ በኋላ አይደለም፤ (ዘፍ 22፥12፤ዘኍ3፥39-51 ይመ፤ ከሮሜ 12፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

*13፥14፤* የ12፥26 ማብ ይመ።

*13፥16፤* የቍ 9 ማብ ይመ።

ቢሆንም እንኳ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) በፍልስጥ ኤም ምድር በሚያልፈው መንገድ አልመ ራቸውም “ጦርነት ቢያጋጥማቸው ሐሳባቸ ውን ለውጠው ወደ ግብፅ ይመለሱ ይሆ ናል” ብሎአልና:: 18ስለዚህ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ሕዝቡን ዙሪያ በሆነው በምድረ በዳው መንገድ ወደ ቀይ ባሕር[°] መራቸው፤ እስራ ኤላውያንም ለጦርነት ዝግጁ ሆነው ከግብፅ ወጡ:: 19ዮሴፍ፤ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) በእርግጥ ይጐበኛችኋል፤ በዚያን ጊዜም ዐፅሜን ይዛችሁ ከዚች ምድር መውጣት አለባችሁ[″] ብሎ የእስራኤልን ልጆች አስምሎአቸው ስለ ነበር ሙሴ የዮሴፍን ዐፅም ይዞ ወጣ:: እግዚአ ብሔር (ኤሎሂም) ሕዝቡን ዙሪያ በሆነው በምድረ በዳው መንገድ ወደ ቀይ ባህር መራቸው፤ እስራኤላውያንም ለጦርነት ዝግጁ ሆነው ከግብፅ ወጡ::

20እነርሱም ከሱኮት ከተነሡ በኋላ ከም ድረ በዳው ጥግ ባለው በኤታም ሰፈሩ:: 21ስለዚህ በቀንም ሆነ በሌሊት መጓዝ ይችሉ ዘንድ፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) በቀን በመንገ ዳቸው ሊመራቸው በደመና ዓምድ፣ በሌሊት ደግሞ ብርሃን ሊሰጣቸው በእሳት ዓምድ በፊታቸው ይሄድ ነበር:: 22በቀንም ሆነ በሌሊት የደመናውና የእሳቱ ዓምድ ከሕዝቡ ፊት የተለየበት ጊዜ አልነበረም::

14 ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ 2“እስራኤላውያን ተመል ሰው በሚግዶልና በባሕሩ መካከል ባለው በፊሀሒሮት አጠገብ እንዲሰፍሩ ንገራቸው፤ በበኣልዛፎንም አንጻር በባሕሩ አጠገብ ይስ ፈሩ:: 3‘ፈርዖን እስራኤላውያን ግራ ተጋብተው በምድረ በዳ በመቅበዝበዝ ይንከራተታሉ’ ብሎ ያስባል:: 4እኔም የፈርዖንን ልብ ስለ ማደነድነው ያሳድዳቸዋል፤ ነገር ግን በፈር ዖንና በሰራዊቱ ሁሉ ለራሴ ክብርን አገኛለሁ፤ ግብፃውያንም እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) መሆኔን ያውቃሉ::” እስራኤላውያንም ይህንኑ አደረጉ::

5የግብፅ ንጉሥ ሕዝቡ መሄዳቸው በተነ ገረው ጊዜ፣ ፈርዖንና ሹማምንቱ ስለ እነ ርሱ የነበራቸውን አሳብ በመለወጥ፣ “ምን ማድረጋችን ነው? እስራኤላውያን እንዲሄዱ ለቀቅናቸው፤ አገልግሎታቸውንም አጣን” አሉ:: 6ስለዚህ ሠረገላው እንዲዘጋጅለት አደረገ፤ ሰራዊቱንም ይዞ ተንቀሳቀሰ:: 7ስድ ስት መቶ ምርጥ ሠረገላዎችን ከሌሎች የግብፅ ሠረገላዎች ጋር ከነጦር አዛዦቻ ቸው አሰልፎ ተነሣ:: 8እግዚአብሔር (ያህዌ) የንጉሡን የፈርዖንን ልብ ስለ አደነደነው በልበ ሙሉነት ከግብፅ የሚወጡትን እስራ ኤላውያን አሳደዳቸው:: 9ግብፃውያን፣ ይኸ ውም የፈርዖን ፈረሶችና ሠረገላዎች፣[w] ፈረሰኞችና እግረኞች ሁሉ እስራኤላውያንን አሳደዷቸው፤ በበአልዛፎን አንጻር በባሕሩ አጠገብ በፊሀሒሮት ሰፍረው ሳሉ ደረሱባ ቸው::

10ፈርዖን በቀረበ ጊዜ እስራኤላውያን ቀና ብለው ተመለከቱ፤ እነሆ፣ ግብፃውያን ይከታተሏቸው ነበር፤ እነርሱም በታላቅ ፍር ሃት ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጮኹ:: 11እነ ርሱም ሙሴን እንዲህ አሉት፤ “በምድረ በዳ እንድንሞት ያመጣኸን በግብፅ መቃ ብር ቦታ ጠፍቶ ነውን? ከግብፅ አውጥተህ ምን አደረግህልን? 12በግብፅ ሳለን፣ ‘ተወን እባክህ፤ ግብፃውያንን እናገልግል’ አላልንህም ነበርን? በምድረ በዳ ከምንሞት ግብፃውያንን ብናገለግል ይሻል ነበር!”

13ሙሴም ለሕዝቡ መለሰላቸው፤ “አትሸ በሩ፣ጸንታችሁ ቁሙ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ዛሬ የሚያደርግላችሁን መታደግ ታያላችሁ፤ ዛሬ የምታዩአቸውን ግብፃውያንን ዳግም አታዩአቸውም:: 14እግዚአብሔር (ያህዌ) ስለ እናንተ ይዋጋል፤ እናንተ ያለባችሁ መታገሥ ብቻ ነው::

13፥18 ዘፀ15፥22፤ ኢሱ1፥14፤4፥13፤ መዝ136፥16፤ ሕዝ20፥10
13፥19 ዘፍ47፥29-30፤ኢሱ24፥32፤ሐሥ 7፥16፤ዕብ11፥22
13፥20 ዘፀ12፥37፤ ዘኍ33፥6
13፥21 ዘፀ 14፥19: 24፤24፥16፤33፥9-10፤32፥1፤33፥14፤ 34፥5፤40፥38፤ ዘኍ9፥16፤12፥5፤14፥ 14፤ዘዳ1፥33፤2፥7፤ 31፥8፤መሳ4፥14፤ 5፥4፤ ነህ9፥12:19፤ መዝ68፥7፤77፥20፤ 78፥14፤99፥7፤ 105፥39፤ኢሳ4፥5፤ ኤር2፥2፤ ዕን3፥13፤ 1ቆሮ10፥1፤13፥22
14፥2 ቍ9፤ ዘኍ 33፥7፤ኤር44፥1፤ ሕዝ29፥10
14፥4 ቍ8:17:23፤ ዘፀ4፥21፤6፥2፤9፥16፤ መዝ71፥11፤ሕዝ32፥15፤ሮሜ9፥17:22-23
14፥5 ዘፍ31፥21፤ መዝ105፥25
14፥7 ዘፀ15፥4
14፥8ዘፀ11፥10፤ዘኍ 33፥3፤ሐሥ13፥17
14፥9 ቍ2:6-7:25 ዘፍ47፥17፤ዘፀ15፥9፤ ኢሱ24፥6፤ኢሳ43፥17
14፥10 ዘፀ15፥25፤ ኢሱ24፥7፤ነህ9፥9፤ መዝ5፥2፤34፥17፤ 50፥15፤107፥6:28
14፥11 ዘፀ5፥21፤ 16፥3፤17፥3፤ዘኍ11፥ 1፤14፥22፤20፥4፤ 21፥5፤ዘዳ9፥7 መዝ106፥7-8
14፥12 ዘፀ5፥21፤ 15፥24፤17፥2፤ መዝ106፥7-8
14፥13 ቍ30፤ ዘፍ15፥1፤1ሳሙ 12፥16፤ 2ዜና20፥17
14፥14 ቍ25፤ ዘፀ15፥3፤ዘዳ1፥30፤ 3፥22፤20፥4፤ኢሱ

°18 በዕብራይስጡ ያሙሱፍ ይላል:: ትርጕሙም የሸምበቆ ባሕር ማለት ነው::
″19 ዘፍ50፥25 ይመ::
w9 በዚህ ስፍራና በቍ 17:18:23 እንዲሁም በቍ 28 ሠረገለኞ ተብሉ ሊተረጉም ይችላል::

13፥17 *በፍልስጥኤም ምድር በሚያልፈው መንገድ፤* ከጌርሳም ወደ ከነዓን ለመሄድ ትክክለኛው መንገድ ቢሆንም መንገዱ የግብፃውያን ምሽግ ነው::

13፥18 *በምድረ በዳው መንገድ፤* በስተ ደቡብ በኩል ወደ ሲና ባሕረ ሰላጤ የሚወስድ መንገድ ነው:: *ቀይ ባሕር፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል “ያም ሱፍ” ይላል፤ ትርጕሙም “የቄጤማ ባሕር” ማለት ነው:: እስራኤላውያን ቀይ ባሕርን ያቋረጡት የት ቦታ እንደ ሆነ በርካታ አስተያየቶች ተሰ ጥተዋል፤ ከአስተያየቶቹ አንዱ በአሁኑ ጊዜ የስዊዝ ቦይ የሚገኝ በት አካባቢ ነው:: *ለጦርነት እንደተዘጋጁ፤* ምናልባት የታጠቁት ጦርና ቀስት ብቻ ሳይሆን አይቀርም::

*13፥19፤* የዘፍ 50፥24-25 ማብ ይመ::

13፥20 *ሱኮት፤* የ12፥37 ማብ ይመ:: *በኤታም፤* ቦታው የት እንደሚገኝ በትክክል አይታወቅም::

13፥21 *በደመና ዓምድ … በእሳት ዓምድ፤* የእግዚአብሔ ርን በሕዝቡ መካከል መገኘት በተጨባጭ የሚገልጽ ምልክት ነው፤ (14፥24 ይመ፤ እንዲሁም የ3፥2 ማብ ይመ):: እግዚአብሔር አብዛኛውን ጊዜ ለሕዝቡ የሚናገረው በደመና ዓምድ ውስጥ ሆኖ ነው (ዘኍ 12፥5-6፤ ዘዳ 31፥15-16፤ መዝ 99፥6-7)::

14፥2 *ተመልሰው፤* የተመለሱት ወደ መጡበት ወደ ደቡብ ነው:: *ፊሃሒሮት፤* “በባዓልዛፎን በስተ ምሥራቅ” የሚገኝ ስፍራ ነው፤ (ዘኍ 33፥7):: *በሚግዶልና፤* ቦታው ወዴት እንደ ሆነ በትክክል አይታወቅም:: የስሙ ትርጕም “ከተማ ጠባቂ” ማለት ነው:: *በባሕር፤* የ13፥18 ማብ ይመ:: የመቃ ተክል ተጨዋማ ውሃ አካባቢ ስለማይበቅል ይህ ቦታ የሚገኘው በስዊዝ ባሕረ ሰላጤ አካባቢ ነው የሚለውን አስተያየት እንዳንቀበል ያደርገ ናል:: ከዚህ በተጨማሪ አንድ የግብፅውያን የጥንት ጽሑፍ ባዓ ልዛፎን ከራምሴ በስተምሥራቅ 32 ኪሎ ሜትር ርቆ በሚገኘው፣ በሜንዛሌህ ሐይቅ አካባቢ በጣፌናስ (የኤር 2፥16 ማብ ይመ) ግዛት ውስጥ እንደምትገኝ ይናገራል:: ስለዚህ እስራኤላውያን ቀይ ባሕርን የተሻገሩት በሜንዛሌህ ሐይቅ ደቡባዊ ጫፍ ላይ ሳይሆን አይቀርም:: *በዓልዛፎን፤* ትርጕሙ “የሰሜኑ በዓል” ወይም “የሰሜኑ ተራራ በዓል” ማለት ነው:: በዓል የከነዓናውያን አምላክ ስም ነው::

14፥4 *እኔ እግዚአብሔር መሆኔን ያውቃሉ፤* የ6፥3 ማብ ይመ::

14፥7 *ከነ ጦር አዛዦቻቸው፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገ ባው የዕብራይስጡ ቃል “ሦስተኛው ሰው” የሚል ትርጕም አለው፤ ይህም ምናልባት ሠረገላውን ከሚነዱ ሰዎች መካከል የአዛዡ ቦታ የት እንደ ሆነ ያመለክታል::

14፥14 *እግዚአብሔር ስለ እናንተ ይዋጋል፤* ምንም እንኳ እስራኤል “ለጦርነት ብትዘጋጅ”፣ (13፥18) ደግሞም “በድፍረት




የእስራኤላውያን ከግብፅ ምድር መውጣት በግብፃውያን የታሪክ ጸሐፍት ቸል ተብሎአል:: የግብፅ ሐውልቶች ይህን ታሪክ በቀጥታ ባይጠቅሱትም የፈርዖን-ሜርኔፍታ ሐውልት (1225 ዓ.ቅ.ክ ገደማ) እስራኤል በመባል ከሚጠራ ሕዝብ ጋር በከነዓን ሰሜናዊ ክፍል የግብፅ ሠራዊት እንደ ተዋጋ ያመለክታል::

እርግጠኛ የሆነ መልክአ ምድራዊና የዘመን ቅደም ተከተልን የሚያመለክት ማስረጃ ማግኘት አስቸጋሪ ቢሆንም እጅግ ብዙ ከሆኑ የጥንት ግኝቶች ስብርባሪዎች እና ጽሑፎች አዲስ መረጃ ተገኝቷል:: የሒታውያን የጥንት ጽሑፍ እግዚአብሔር ከእስራኤል ሕዝብ ጋር በሲና ተራራ ከገባው ኪዳን ጋር ተመሳሳይነት አለው::

የነሐስ ዘመን የመጨረሻው ክፍል (1550-1200 ዓ.ቅ.ክ) በሕዝብ ፍልሰት ይታወቃል:: በምሥራቃዊው የአባይ ክፍል በሴማውያን ላይ የነበረው የግብፅ አገዛዝ በጡብ ሥራ ጫና በመፍጠር፣ ከባድ የጉልበት ሥራ በማሠራትና የእርሻ መሬት የሌላቸውን በዝቅተኛ የኑሮ ደረጃ ያሉትን በማስጨነቅ ይታወቅ ነበር:: አያሌ የከነዓናውያን ከተሞች በጭካኔ ወድመዋል:: የባሕር ሰዎች በመባል የሚታወቁትን ጨምሮ አዳዲስ ሕዝቦች በግብፅ፣ በፍልስጥኤም፣ በዮርዳኖስ ማዶና በምሥራቃዊው ሜድትራንያን ሰፈሩ::

በአክናተን ዘመን (1375 ዓ.ቅ.ክ ገደማ) ከከነዓን ከተሞች ገዥዎች ወደ ግብፃውያን መንግሥት ይደረግ የነበረው የመልእክት ልውውጥ ከግብፅ ሠራዊት ጋር የነበረውን ደካማ የግንኙነት መዋቅር የሚያመለክት ሲሆን፣ «ሐቢሩ» በመባል የሚታወቀውን ሕዝብ እጅግ ይፈሩት እንደነበርም ይጠቀማል::

[15]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "ለምን ትጮኹብኛላችሁ? ይልቅስ እስራኤላውያንን ወደፊት እንዲጓዙ ንገራቸው፤ [16]ውሃውን ለመክፈል በትርህን አንሣና እጅህን በባሕሩ ላይ ዘርጋ፤ እስራኤላውያን በባሕሩ ውስጥ በየብስ ይሻገራሉ:: [17]ተከትለዋቸው እንዲገቡም የግብፃውያንን ልብ አጸናለሁ፤ በፈርዖንና በሰራዊቱ ሁሉ፣ በሠረገሎቹና በፈረሰኞቹ ለራሴ ክብርን አገኛለሁ:: [18]በፈርዖንና በሰራዊቱ ሁሉ፣ በከበርሁ ጊዜ ግብፃውያን እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደሆንሁ ያውቃሉ::

[19]ከዚያም ከእስራኤል ሰራዊት ፊት ፊት ሆኖ ሲሄድ የነበረው የእግዚአብሔር (ኤሎሂም) መልአክ ተመለሰና ወደ ኋላቸው መጣ፤ የደመናውም ዓምድ እንዲሁ ከፊት ተነሥቶ ከኋላቸው ቆመ፤ [20]በግብፅና በእስራኤል ሰራዊት መካከል በመሆን፣ ሌሊቱን ሙሉ ደመናው በአንድ በኩል ጨለማን ሲያመጣ፣ በሌላው በኩል ብርሃን አመጣ፤ ስለዚህ ሌሊቱን በሙሉ አንዱ ወደ ሌላው ሊጠጋ አልቻለም::

[21]ሙሴ እጁን በባሕሩ ላይ ዘረጋ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሌሊቱን በሙሉ ብርቱ የምሥራቅ ነፋስ አስነሥቶ ባሕሩን ወደ ኋላ በማሸሽ ደረቅ ምድር አደረገው፤ ውሃው ተከፈለ፤ [22]እስራኤላውያን ውሃው በግራና በቀኝ እንደ ግድግዳ ሆኖ በየብስ በባሕሩ ውስጥ አለፉ::

[23]ግብፃውያንም አሳደዷቸው፤ የፈርዖን ፈረሶች፣ ሰረገሎችና ፈረሰኞች በሙሉ ተከትለዋቸው ወደ ባሕሩ ገቡ:: [24]ሲነጋጋም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በእሳትና በደመና ዓምድ ሆኖ በግብፃውያን ሰራዊት ሽብር ላከባቸው:: [25]መንዳት እንዳይችሉም የሠረገላዎቹን መሽከርከሪያዎች አቈላለፈባቸው[f] ግብፃውያኑም፣ "ከእስራኤላውያን እንሽሽ! *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ግብፅን እየተዋጋላቸው ነው" አሉ::

[26]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን፣ "ውሃው ግብፃውያንን ሠረገሎቻቸውንና ፈረሰኞቻቸውን ተመልሶ እንዲሸፍናቸው እጅህን በባሕሩ ላይ ዘርጋ" አለው:: [27]ሙሴም እጁን በባሕሩ ላይ ዘረጋ፤ ንጋት ላይም ባሕሩ ወደ ቀድሞ ቦታው ተመለሰ:: ግብፃውያን ከውሃው ሸሹ፤[g] *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ግብፃውያንን በባሕሩ ውስጥ ጣላቸው:: [28]ውሃውም ተመልሶ እስራኤላውያንን ተከትለው ወደ ባሕሩ የገቡትን ሠረገሎች፣ ፈረሰኞች፣ መላውን የግብፅ ሰራዊት ሁሉ ሸፈነ:: አንድም እንኳ አልተረፈም::

[29]እስራኤላውያን ግን ውሃው ግራና ቀኝ እንደ ግድግዳ ሆኖ፣ በደረቅ ምድር ባሕሩን ተሻገሩ:: [30]በዚያች ዕለት *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እስራኤልን ከግብፃውያን እጅ አዳናቸው፤ እስራኤልም የግብፃውያን ሬሳ በባሕሩ ዳርቻ ወድቆ ተመለከቱ:: [31]እስራኤላውያን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በግብፃውያን ላይ ያደረገውን ታላቅ ኀይል ባዩ ጊዜ፣ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ፈሩ፤ *በእግዚአብሔርና* (ያህዌ)፣ በባሪያው በሙሴም አመኑ::

### የሙሴና የማርያም መዝሙር

**15** ከዚያም ሙሴና እስራኤላውያን ይህን መዝሙር *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘመሩ፤

10፥14፤23፥3:10፤ 1ሳሙ 12፥16፤2ሳሙ 5፥24፤2ዜና 20፥29፤ ነህ 4፥20፤መዝ 24፥8፤ 35፥1፤37፥7፤46፥10፤ 116፥7፤ኢሳ 42፥13፤ 28፥12፤30፥15፤ኤር 41፥12፤ሕዝ 32፥15፤ ዘካ 2፥13
14፥15 ኢሱ 7፥10
14፥16 ቍ 27፤ዘፀ 4፥2፤ኢሳ 10፥26
14፥17 ቍ 4፤ ዘፀ 4፥21
14፥18 ዘፀ 6፥2፤ ሕዝ 32፥15
14፥19 ዘፍ 16፥7፤ ዘፀ 13፥21፤ኢሳ 26፥7፤ 42፥16፤49፥10፤ 52፥12፤58፥8፤63፥9፤ 1ቆሮ 10፥1
14፥20 ኢሱ 24፥7
14፥21 ቍ 22፤ዘፍ 8፥1፤41፥6፤ዘፀ 4፥2፤ 7፥19፤15፥8፤2ሳሙ 22፥16፤1ነገ 19፥11፤ 2ነገ 2፥8፤ኢዮ 26፥12፤ 38፥1፤40፥6፤መዝ 74፥13፤78፥13፤114፥5፤136፥13፤ኢሳ 14፥27፤23፥11፤51፥15፤ 63፥12፤ኤር 31፥35፤ ኤር 23፥19፤ናሆ 1፥3፤ ሐሥ 7፥36
14፥22 ቍ 7:16: 21፥29፤ዘፀ 3፥12፤ 15፥8:19፤ዘኍ 33፥8፤ ዘዳ 31፥6-8፤ ኢሱ 3፥13:16-17፤ 4፥22፤24፥6፤ ነህ 9፥11፤መዝ 66፥6፤ 77፥19፤78፥13፤ 106፥9፤ ኢሳ 11፥15፤41፥10፤ 43፥5:16፤44፥27፤ 50፥2፤51፥10፤63፥11:13፤ኤር 46፥28፤ ናሆ 1፥4፤ዕብ 11፥29 1ቆሮ 10፥1
14፥23 ቍ 7
14፥24 ዘፀ 13፥21፤ 23፥27፤ኢሱ 10፥10፤ 1ሳሙ 5፥9፤7፥10፤
14፥15፤2ሳሙ 5፥24፤2ነገ 7፥6፤19፥7፤1ቆሮ 10፥1 14፥25 ቍ 9:14፤ ዘዳ 32፥31፤1ሳሙ 2፥2፤4፥8 14፥27 ቍ 28፤ዘፀ 15፥1:21፤ዘዳ 1፥40፤ 2፥1፤11፥4፤ኢሱ 4፥18፤መዝ 78፥53፤106፥11፤136፥15፤ዕብ 11፥29
14፥28 ቍ 23:27፤ዘፀ 15፥5:19፤ኢሱ 24፥7፤መሳ 4፥16፤ነህ 9፥11
14፥29 ቍ 21:22፤ 2ነገ 2፥8፤ኢሳ 24፥11፤ መዝ 74፥15፤78፥13
14፥30 ቍ 29፤1ሳሙ 14፥23፤1ዜና 11፥14፤መዝ 44፥7፤106፥8:10: 21፤ኢሳ 43፥3፤50፥2፤51፥9-10፤60፥16፤63፥8:11 14፥31 ዘፀ 4፥5፤ 9፥16፤20፥18፤ዘዳ 31፥13፤ኢሱ 4፥24፤1ሳሙ 12፥18፤መዝ 22፥4፤40፥3፤ 76፥7፤106፥12፤112፥1፤147፥5፤ዮሐ 2፥11፤11፥45 15፥1 ዘፀ 14፥27 ፤ዘኍ 21፥17፤ዘዳ 11፥4፤መሳ 5፥1:3፤2ሳሙ 22፥1፤1ዜና 16፥9፤ኢዮ 36፥24፤መዝ 13፥6፤21፥13፤27፥6፤61፥8፤76፥6፤59፥16፤104፥33፤ 105፥72፤106፥12፤ኢሳ 12፥5:6፤42፥10፤44፥23፤ኤር 51፥21

[f]25 ወይም፤ *ወደ ሠረገላዎቻቸው መንኰራኵር ዘለሉ* ተብሎ ሊተረጐም ይችላል እሬተ ሳምራውያን የሰብዓ ሊቃናትና የሱርስት ትርጕሞችን ይመ::
[g]27 ወይም፣ *ወደ ውሃው ሸሹ*

ብትወጣም" (ቍ 8) ድሉ የእግዚአብሔር ብቻ ነው::

14፥19 *የእግዚአብሔር መልአክ፤* የዘፍ 16፥7 ማብ ይመ:: እዚህ ላይ "የእግዚአብሔር መልአክ" የሚለው የተያያዘው ከደመና ጋር ነው፤ (13፥21 ይመ)::

14፥20 *በግብፅና በእስራኤል መካከል በመሆን፤* የደመናው ዐምድ (የእግዚአብሔርን መገኘት ያመለክታል) እስራኤልን ይከልልና ይጠብቅ ነበር፤ (መዝ 105፥39 ይመ)::

14፥21 *ብርቱ የምሥራቅ ነፋስ፤* 10፥13 ይመ:: በ15፥8 ላይ ዘማሪው እግዚአብሔርን እያመሰገነ ነፋሱን "የአፍንጫህ እስትንፋስ" በማለት ይጠራዋል፤ በሁለቱም ቦታዎች ላይ እንደምናነበው ታምሩ የተፈጸመው በእግዚአብሔር ጊዜና አመራር ነው (15፥10 ይመ)::

14፥22 *በየብስ፤* መዘምራንና ነቢያት እግዚአብሔር ለእስራኤል ምን እንዳደረገ ያስታውሷት ነበር፤ (መዝ 66፥6፤ 106፥9፤ 136፥13-14፤ ኢሳ 51፥10፤63፥11-13 ይመ):: *ውሃው ... እንደ ግድግዳ ሆኖ፤* ቍ 29 ይመ:: ውሃው በግራና በቀኝ "ወደ ላይ ተቆለለ" (15፥8)::

14፥24 *ሲነጋም፤* አብዛኛውን ጊዜ ድንገተኛ አደጋ የሚደርሰው በዚህ ጊዜ ነው፤ (ኢሱ 10፥9፤ 1ሳሙ 11፥11 ይመ):: *እግዚአብሔር ... በተመለከተ ጊዜ፤* የ13፥21 ማብ ይመ::

14፥25 *እግዚአብሔር ... እየተዋጋላቸው፤* የቍ 14 ማብ ይመ::

14፥27 *እግዚአብሔር ... በባሕር ውስጥ ጣላቸው፤* ስምንተኛውን መቅሠፍት በግብፃውያን ላይ ባወረደ ጊዜ፣ አንበጣዎቹን በባሕር ውስጥ እንደጨመራቸው ሁሉ፣ አሁን ደግሞ ግብፃውያንን በዚያው ባሕር ውስጥ ጠራርጎ አዳፈናቸው፤ (10፥19 ይመ)::

14፥28 *አንድም እንኳ አልተረፈም፤* እግዚአብሔር በፈርዖን ሰራዊት ላይ የተቀዳጀው ድል ሙሉ ነበር::

14፥31 *እግዚአብሔርን ፈሩ፤* የዘፍ 20-11 ማብ ይመ:: *በእግዚአብሔርና በሙሴ አመኑ፤* አሁን እስራኤላውያን በእግዚአብሔር ብርቱ ኀይልና በሙሴ አመራር መታመን ጀመሩ:: *በባሪያው፤* እዚህ ላይ ቃሉ የሚያመለክተው በእግዚአብሔር ንጉሣዊ አስተዳደር ውስጥ ከፍተኛ ሥልጣን ያለውን ሰው ነው፤ (ዘኍ 12፥8፤ ዘዳ 34፥5 ይመ):: ይህ መጠሪያ ለኢያሱ (ኢሱ 24፥29)፣ ለሳሙኤል (1ሳሙ 3፥10)፣ ለዳዊትና (2ሳሙ 3፥18) ለኤልያስ (2ነገ 9፥36) እንደ ተሰጠ ይመ::

*15፥1-18፤* እግዚአብሔር በፈርዖንና በሰራዊቱ ላይ የተቀዳጀውን ታላቅ ድል የሚገልጽ መዝሙር ነው:: መዝሙሩ የሚያተኵረው በራሱ በእግዚአብሔር ላይ ነው፤ (ቍ 11 ይመ)፤ እግዚአብሔር የሚለው መለኮታዊ ስም ዐሥር ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል:: ንጽጽሮች "እንደ ድንጋይ" (ቍ 5)፣ "እንደ ግድግዳ" (ቍ 8)፣ "እንደ ብረት" (ቍ 10) የመሳሰሉት ከአምስቱ የመዝሙሩ አንጓዎች ውስጥ ለሦስቱ እንደ መደምደሚያ ያገለግላሉ:: የመጀመሪያዎቹ አራት አንጓዎች (ቍ 1-5:6-8:9-10:11-12) በቀይ ባሕር ላይ እግዚአብሔር ሕዝቡን እንዴት "እንደታደገ" (14፥13) አንድ በአንድ ይተርካሉ፤ የመጨረሻው አንጓ (ቍ 13-18) በከነዓን ስለሚጠብቃቸው ተጨማሪ ድል ይናገራል::

15፥1 *ሙሴና የእስራኤል ልጆች ... ዘመሩ፤* እንደ አንድ

"ከፍ ከፍ ብሎ ከብሮአልና፣
ለእግዚአብሔር (ያህዌ) እዘምራለሁ፤
ፈረሱንና ፈረሰኛውን፣
በባሕር ውስጥ ጥሎአልና::
[2]እግዚአብሔር (ያህዌ) ብርታቴና
ዝማሬዬ ነው፤
ድነቴም ሆነልኝ፤
እርሱ አምላኬ ነው፤
አመሰግነዋለሁ፤
የአባቴ አምላክ (ኤሎሂም) ነው፤ እኔም
ከፍ ከፍ አደርገዋለሁ::
[3]እግዚአብሔር (ያህዌ) ተዋጊ ነው፤
ስሙም እግዚአብሔር (ያህዌ) ነው::
[4]የፈርዖንን ሠረገሎችና ሰራዊት፣
ባሕር ውስጥ ጣላቸው፤
ምርጥ የሆኑት የፈርዖን ሹማምንት፣
ቀይ ባሕር ውስጥ ሰጠሙ::
[5]ቀላያትንም ለበሱ፤
እንደ ድንጋይ ወደ ጥልቁ ወረዱ::
[6]"አቤቱ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤
ቀኝ እጅህ በግርማ ከበረ፤
አቤቱ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤
ቀኝ እጅህ ጠላትን አደቀቀ::
[7]በግርማህ ታላቅነት፣
የተቃወሙህን ጣልኻቸው፤
ቍጣህን ሰደድህ፤
እንደ ገለባም በላቸው::
[8]በአፍንጫህ እስትንፋስ፣ ውሆች ተቈለሉ፤
ፈሳሾችም እንደ ግድግዳ ቆሙ፤
የጥልቁ ውሃ ባሕሩ ውስጥ ረጋ::
[9]"ጠላት፣
'አሳድዳቸዋለሁ፤ እማርካቸዋለሁ፤
ምርኮን እካፈላለሁ፤
ነፍሴ በእነርሱ ትጠግባለች፤
ሰይፌን እመዛለሁ፤
እጄም ትደመስሳቸዋለች' አለ::
[10]አንተ ግን እስትንፋስህን አነፈስህ፤
ባሕርም ከደናቸው፤
በኃያላን ውሆች፣
እንደ ብረት ሰጠሙ::

15፥2 ዘፍ28፥21፤ 45፥7፤ዘዐ14፥13፤ዘዳ 10፥21፤2ሳሙ22፥47 ፤መዝ18፥1:2:46፤ 22፥3፤25፥5፤27፥1፤ 30፥1፤34፥3፤35፥27፤ 59፥17፤62፥2፤99፥5፤ 103፥19፤107፥32፤ 108፥5፤109፥1፤118፥ 14:28፤145፥1፤148 ፥14፤ኢሳ12፥2፤24፥ 15፤25፥1፤ኤር17፥14 ፤ዳን4፥37፤ዮና2፥9፤ ዕን3፥18
15፥3 ዘዐ3፥15፤ 14፥14፤ራእ19፥11
15፥4 ዘዐ14፥6-7፤ ኤር51፥21
15፥5 ቍ10፤ ዘዐ14፥28፤ነህ9፥11
15፥6 ዘዐ3፥20፤ ዘኍ24፥8፤1ሳሙ2፥ 10፤ኢዮ40፥14፤ መዝ2፥9፤16፥11፤ 17፥7፤21፥8፤63፥8፤ 74፥11፤77፥10፤ 89፥13፤98፥1፤ 118፥15፤138፥7
15፥7 ዘዐ24፥17፤ ዘዳ4፥24፤9፥3፤33፥ 26፤መዝ2፥5፤18፥8፤ 59፥13፤78፥49-50፤ 150፥2፤ኤር12፥13፤ 25፥38፤ዕብ12፥29
15፥8 ዘዐ14፥21: 22፤ኢሱ3፥13፤ መዝ18፥15፤46፥2፤7 8፥13፤ኢሳ43፥16
15፥9 ዘዐ14፥5-9፤ ዘዳ28፥45፤መሳ5፥ 30፤መዝ7፥5፤ ኢሳ9፥3፤53፥12፤ ሰቆ1፥3፤ሉቃ11፥22
15፥10 ቍ5፤ኢዮ 4፥9፤15፥30፤ነህ9፥11 ፤መዝ29፥3፤32፥6፤77 ፥19፤ኢሳ11፥4፤ 30፥33፤40፥7
15፥11 ዘዐ3፥20፤ 8፥10፤14፥4፤ዘሌ19፥ 2፤1ሳሙ2፥2፤1ዜና 16፥29፤መዝ4፥2፤8፥ 1፤26፥8፤77፥13፤99፥ 3፤110፥3፤ኢሳ6፥3፤ 35፥2፤40፥5፤46፥5፤ ራእ4፥8
15፥12 ዘዐ7፥5፤

[11]"አቤቱ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤
ከአማልክት መካከል፣
እንደ አንተ ማን አለ?
በቅድስናው የከበረ፣
በክብሩ የሚያስፈራ፣
ድንቆችን የሚያደርግ፣
እንደ አንተ ማን አለ?
[12]ቀኝ እጅህን ዘረጋህ፤
ምድርም ዋጠቻቸው::
[13]"በማይለወጠው ፍቅርህ፣
የተቤዠኻቸውን ሕዝብህን ትመራለህ፤
እነርሱን በብርታትህ፣
ወደ ቅዱስ ማደሪያህ ትመራቸዋለህ::
[14]አሕዛብ ይሰማሉ፤ ይንቀጠቀጡማል፤
የፍልስጥኤምን ሕዝብ ሥቃይ
ይይዛቸዋል::
[15]የኤዶምም አለቆች ይርዳሉ፤
የሞአብ አለቆች በእንቅጥቃጤ ይያዛሉ፤
በከነዓን ሕዝብ ይቀልጣሉ::
[16]አቤቱ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤ ሕዝብህ
እስከሚያልፉ ድረስ፣
የተቤዠኻቸው ሕዝብህ እስኪያልፉ ድረስ፣
ድንጋጤና ሽብር በእነርሱ ላይ ይመጣል፤
በክንድህ ብርታት፣
እንደ ድንጋይ የማይንቀሳቀሱ
ይሆናሉ::
[17]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤ ማደሪያህ
እንዲሆን በሠራኸው ስፍራ፣
ጌታ ሆይ (አዶናይ)፤ እጆችህ በሠሩት
መቅደስ፣
በርስትህ ተራራ ላይ፣

ዘኍ16፥32፤26፥10፤ዘዳ11፥6፤መዝ106፥17 15፥13 ቍ17፤ዘዐ6፥6፤ ነህ9፥12፤ኢዮ33፥28፤መዝ68፥16፤71፥23 ፤76፥2፤77፥20፤ 78፥54፤ 106፥10፤ኢሳ1፥27፤41፥14፤43፥14፤44፥22-24፤51፥10፤63፥9፤ ቲቶ2፥14 15፥14 ቍ16፤ዘዐ23፥27፤ዘዳ2፥25፤ኢሱ2፥9፤5፥1፤ 9፥24፤1ሳሙ4፥7፤አስ8፥17፤መዝ48፥6፤83፥7፤96፥9፤99፥1፤ 114፥7፤ኢሳ13፥8፤ሕዝ38፥20፤ 15፥15 ዘፍ36፥15፤ዘኍ22፥3፤ ዘዳ2፥4፤ኢሱ2፥9:24፤መዝ114፥7 15፥16 ቍ14፤ዘፍ35፥5፤ዘዳ2፥4፤ 1ሳሙ25፥37፤መዝ74፥2፤2ጴጥ2፥1 15፥17 ቍ13፤ዘዐ23፥20፤ 32፥34፤33፥12፤ዘዳ33፥19፤2ሳሙ7፥10፤መዝ2፥6፤3፥4፤15፥1፤44፥2፤ 78፥54:68:69፤80፥8:15፤114፥2፤132፥13-14፤133፥3፤ኢሳ5፥2፤ 60፥21፤ኤር2፥21፤11፥17፤24፥6፤ዳን9፥16፤ኢል2፥1፤አሞ9፥15፤ አብ1፥16፤ሰፎ3፥11፤

ሰው ሆኖ መላው የእስራኤል ሕዝብ እግዚአብሔርን አመሰገነ:: *እዘምራለሁ፤* የተለመደ የምስጋና መዝሙሮች መግቢያ ነው፤ (መሳ 5፥3፤ መዝ 89፥1፤ 101፥1፤ 108፥1 ይመ):: 15፥2፤ የዚህ ቍጥር የመጀመሪያው ክፍል በመዝ 118፥14 ላይ ቃል በቃል ተጠቅሶአል፤ (ኢሳ 12፥2 ይመ)::

15፥3 *እግዚአብሔር ተዋጊ ነው፤* የ14፥14 ማብ ይመ:: በውጊያ ላይ የእግዚአብሔርን ሕዝብ እንደ ንጉሥ ሆኖ የሚመራ እግዚአብሔር ነው፤ (ዘዳ 1፥30፤ መሳ 4፥14፤ 2ሳሙ 5፥24፤ 2ዜና 20፥17-18 ይመ)::

15፥4 *የፈርዖን ሹማምንት፤* የ14፥7 ማብ ይመ::

15፥5 *እንደ ድንጋይ ወደ ጥልቅ ወረዱ፤* በኤር51፥63-64 ላይ የባቢሎን ዕጣ ፈንታ ይህንን እንደሚመስል ተገልጾአል::

*15፥8፤* የ14፥22 ማብ ይመ:: *በአፍንጫህ እስትንፋስ፤* የ14፥21 ማብ ይመ:: እንዲሁም መዝ 18፥15 ይመ::

15፥10 *እስትንፋስህን አነፈሀ፤* የ14፥21 ማብ ይመ::

15፥11 *እንደ አንተ ማን አለ?* መዝ35፥10፤ 71፥19፤ 89፥6፤ 113፥5፤ሚኪ7፥18 ይመ:: ተቀናቃኞቹን ከቶ የማይታገሥ አምላክ የግብፅን አማልክትና አምላኪዎቻቸውን በሙሉ ድል አደረገ::

15፥12 *ምድር፤* ግብፃውያንን የዋጠው ባሕሩ በመሆኑ ይህ ቃል ምናልባት የሚያመለክተው፣ "የሙታን ዓለም" (ዘዳ 32፥22) የሆነ ውን ሲአልን ወይም መቃብርን ነው፤ (መዝ63፥9፤71፥20 ይመ)::

15፥13 *የተቤዠኻቸውን ሕዝብህን፤* የ6፥6 ማብ ይመ:: *ቅዱስ ማደሪያህ፤* ምናልባት በሴሎ የሚገኘውን የማምለኪያ ቤት (ኤር 7፥12 ይመ) እንዲሁም በጽዮን ተራራ (መዝ 76፥2 ይመ) ማለትም እግዚአብሔር በመረጠው ስፍራ የሚሠራውን ቤተ መቅደስ የሚያመለክት ቃል ነው፤ (ዘዳ 12፥14:18:26፤ 14፥25፤ 16፥7:15-16፤ 17፥8:10፤ 18፥6፤ 31፥11 ይመ)፤ እግዚአብሔር "ስሙ" እንዲጠራበት የመረጠው ይህንን ስፍራ ነው፤ (ዘዳ 12፥5: 11:21፤14፥23-24፤ 16፥2:6:11፤26፥2):: ነገር ግን ቃሉ "ቅዱስ ማደሪያህ" በቍ 17 ላይ የተጠቀሰችውን የተስፋዪቱንም ምድር ያመለክታል::

15፥14-15 *የፍልስጥኤም ... የኤዶም ... የሞዓብ ... በከነዓን፤* እስራኤላውያን ከሲና ተራራ ተነሥተው ወደ ተስፋዪቱ ምድር የሚያደርጉት ጕዞ በዚህ ቅደም ተከተል መሠረት ይሆናል::

15፥15 *መሪዎች፤* ቀደም ሲል ቃሉ ለኤዶም ገዥዎች ተሰጥቶአል፤ (ዘፍ 36፥15-19:21:29-30:4:43 ይመ)::

15፥16 *ድንጋጤ ... ይመጣል፤* የ1ዜና 14፥17 ማብ ይመ:: *የተቤዠኸው፤* ይህ ቃል "የፈጠርኸው" ተብሎም ሊተረጐም ይችላል፤ ዘዳ 32፥6 ይመ::

15፥17 *ርስት፤* የተስፋዪቱ ምድር ናት (1ሳሙ 26፥19፤

*ታመጣቸዋለህ፤ ትተክላቸዋለህም።*
[18]*እግዚአብሔር* (ያህዌ)፣
ከዘላለም እስከ ዘላለም ይነግሣል።"

[19]የፈርዖን ፈረሶች፣ ሠረገሎቹና[ж] ፈረሰ ኞቹ ወደ ባሕሩ በገቡ ጊዜ *እግዚአብሔር* (ያህዌ)የባሕሩን ውሃ በላያቸው ላይ መለሰባ ቸው፤ እስራኤላውያን ግን በባሕሩ ውስጥ በደረቅ ምድር ተሻገሩ። [20]ከዚያም የአሮን እኅት ነቢይቱ ማርያም ከበሮዋን አንሥታ ያዘች፤ የቀሩትም ሴቶች ሁሉ ከበሮ ይዘው እያሸበሸቡ ተከተሏት።

[21]ማርያምም፣
"ፈረሱንና ፈረሰኛውን፣
በባሕር ውስጥ ጥሎአል፤
*ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘምሩ፤
እጅግ ከፍ ከፍ ብሎአልና"
እያለች ዘመረችላቸው።

## የማራና የኤሊም ውሃ

[22]ከዚያም ሙሴ እስራኤልን ከቀይ ባሕር እየመራቸው ወደ ሱር ምድረ በዳ ሄዱ፤ ለሦስት ቀናት ውሃ ሳያገኙም በምድረ በዳ ተጓዙ። [23]ማራ በደረሱ ጊዜ ውሃው መራራ ስለ ነበር ሊጠጡት አልቻሉም፤ ቦታው ማራ ተብሎ የተጠራውም ከዚህ የተነሣ ነው።[1] [24]ሕዝቡም በሙሴ ላይ በማጕረምረም፣ "ምን እንጠጣ?" አሉ።

[25]ከዚያም ሙሴ ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጮኸ፤ *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) አንዲት ዛፍ አሳየው፤ እርሷንም ወደ ውሃው ጣላት፤ ውሃውም ጣፋጭ ሆነ።

በዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሕግና ሥርዐት አበጀላቸው፤ በዚያም ሥፍራ ፈተና ቸው። [26]እርሱም አለ፤ "የአምላካችሁን *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ድምፅ በጥንቃቄ ብት ሰሙ፣ በፊቱም ትክክል የሆነውን ብትፈ ጽሙ፣ ትእዛዛቱን ልብ ብትሉና ሥርዐቱንም ሁሉ ብትጠብቁ፣ በግብፃውያን ላይ ያመጣ ሁባቸውን ማንኛውንም ዐይነት በሽታ በእናንተ ላይ አላመጣም፤ ፈዋሻችሁ እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነኝና።"

[27]ከዚያም ዐሥራ ሁለት ምንጮችና ሰባ የዘንባባ ዛፎች ወዳሉበት ወደ ኤሊም መጡ፤ እነርሱም በውሃው አጠገብ በዚያ ሰፈሩ።

## መናና ድርጭት

**16** መላው የእስራኤል ማኅበር ከግብፅ በወጡ በሁለተኛው ወር በዐሥራ አምስተኛው ቀን ከኤሊም ተነሥተው በኤ ሊምና በሲና መካከል ወደምትገኘው ወደ ሲን ምድረ በዳ መጡ። [2]በምድረ በዳውም መላው ማኅበር በሙሴና በአሮን ላይ አጕረመረሙ። [3]እስራኤላውያንም እነርሱን እንዲህ አሏቸው፣ "በሥጋ መቀቀያው ምንቸት ዙሪያ ተቀምጠን የፈለግነውን ያህል ምግብ መመገብ በምንችልበት በግብፅ ሳለን፣ ምነው *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) እጅ ሞተን ባረፍነው ኖሮ! እናንተ ግን ይህ ሁሉ ጉባኤ በራብ እንዲያልቅ ወደዚህ ምድረ በዳ አመጣ ችሁን" አሏቸው።

[4]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ "ከሰማይ እንጀራ አዘንብላችኋለሁ። ሕዝቡም በየቀኑ እየወጡ ለዕለት የሚበቃ

15፥18 ዘፍ21፥33፤ መዝ9፥7፤29፥10፤ 55፥19፤66፥7፤80፥1፤ 102፥12፤145፥13፤ ሰቆ5፥19
15፥19 ዘፀ14፥22: 28
15፥20 ቍ 21፤ ዘፍ4፥21፤31፥27፤ ዘፀ2፥4፤ዘኍ12፥1፤ 20፥1፤መሳ4፥4፤1 1፥34፤21፥21፤ 26፥59፤1ሳሙ18፥6፤ 2ሳሙ6፥5:14:16፤ 2ነገ22፥14፤ 1ዜና4፥17፤6፥3፤ 2ዜና34፥22፤ ነህ6፥14፤ መዝ30፥11፤81፥2፤ 149፥3፤150፥4፤ ማሕ6፥13፤ኢሳ8፥3፤ 30፥32፤ኤር31፥4: 13፤ሕዝ13፥17
15፥21 ዘፀ14፥27፤ 1ሳሙ18፥7፤ አሞ2፥15፤ሐጌ2፥22
15፥22 ዘፍ16፥7፤ ዘፀ17፥1:3፤ ዘኍ20፥2:5፤33፥14፤ መዝ78፥52፤107፥5 17፥3፤ዘኍ14፥2፤20፥ 3፤11፥4:34፤ዘዳ8፥3፤ 12፥20፤መዝ78፥18፤ 106፥14፤ኤር44፥17፤
15፥23 ዘኍ33፥8፤ ሩት1፥20
15፥24 ዘፀ14፥12፤ 16፥2፤17፥3፤ዘኍ 14፥2፤ኢሱ9፥18፤ መዝ78፥18:42፤106 ፥13:25፤ሕዝ16፥43፤ ማቴ6፥31
15፥25 ዘፍ22፥1፤ ዘፀ14፥10፤ መሳ3፥4፤ 2ነገ2፥21፤4፥41፤6፥6 ፤ኢዮ23፥10፤መዝ 81፥7፤ኢሳ48፥10
15፥26 ዘፀ19፥5-6፤ 20፥2-17፤23፥22:25- 26፤ዘኍ33፥9፤ ዘዳ7፥12:15፤11፥13፤15፥5፤28፥1፤28፥27:58-60፤32፥39፤1ሳሙ5፥6፤ 2ነገ20፥5፤መዝ25፥11፤30፥2፤41፥3-4፤103፥3፤107፥20፤ኤር11፥6፤ 30፥17፤ሆሴ11፥3፤15፥27
15፥27 ዘኍ33፥9
16፥1 ዘፀ6፥6፤ 12፥1-2፤17፥1፤ዘኍ33፥11:12
16፥2 ዘፀ15፥24፤1ቆሮ10፥10
16፥3 ዘፍ47፥15
16፥4 ቍ14-15፤ዘፍ22፥1፤ዘዳ8፥3፤ነህ9፥15፤ መዝ78፥24፤105፥40፤ዮሐ6፥31

[ж]19 *ወይም፣ ሠረገለኞች*
[1]23 *ማራ ማለት መራራ ማለት ነው*

መዝ 79፥1 ይመ)።

15፥20 *ነቢይቱ፤* ማርያም ስለ ተቀበለችው የነቢይነት ስጦታ የተናገረችውን ቃል በዘኍ 12፥1-2 ላይ እና (የ 7፥1-2 ማብ ይመ)። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የምናገኛቸው ሴት ነቢያት ዲቦራ (መሳ 4፥4)፣ የኢሳይያስ ሚስት (ኢሳ8፥3፤ ማብ ይመ)፣ ሕልዳና (2ነገ 22፥14)፣ ኖዓድያ (ነህ 6፥14)፣ ሐና (ሉቃ 2፥36) እና የፊልጶስ ሴት ልጆች (ሐሥ 21፥9) ናቸው። ሌሎችም ሴቶች ከበ ሮዎቻቸውን እየመቱና እየዘፈኑ ይከተሉአት ጀመር፤ ድል በተገ ኘበት ጦርነት ላይ እንዲህ ያለው ጭፈራና ሆታ የተለመደ ነው፤ (1ሳሙ 18፥6፤ 2ሳሙ 1፥20 ይመ)።

*15፥21፤* እዚህ ላይ ማርያም የድል መዝሙሩን የመጀመ ሪያ አራትስንኞች እንደ ገና ትጠቅሳለች፤ (ቍ 1 ይመ)።

15፥22 *ወደ ሱር ምድረ በዳ፤* ከግብፅ በስተምሥራቅ (ዘፍ 25፥18፤ 1ሳሙ 15፥7 ይመ)፤ ሲና ባሕር ሰርጥ በስተ ሰሜን ምዕራብ የሚገኝ ስፍራ ነው። በዘኍ 33፥8 ላይ "የኤታም በረሓ" ተብሎ ተጠርቶአል። ሱር እንዲሁም ኤታም ማለት "ምሽግ" ማለት ነው፤ (ሱር በዕብራይስጥ ቋንቋ ሲሆን፣ ኤታም ደግሞ በግብፅ ቋንቋ ነው)።

15፥23 *መራራ፤* ምናልባት በአሁኑ ጊዜ በስዊዝ ባሕረ ሰላጤ አካባቢ አይን ሃዋራ ተብሎ የሚጠራው ስፍራ ሳይሆን አይ ቀርም።

15፥24 *በማጕረምረም፤* እስራኤላውያን በምድረ በዳው ጕዞአቸው ላይ ችግር በገጠማቸው ቍጥር፣ በሙሴና በአሮን ላይ ያጕረመርሙ ነበር፤ (16፥2፤ 17፥3፤ ዘኍ 14፥2፤ 16፥11:41)። በእውነት ያጕረመርሙ የነበረው ግን በእግዚአብሔር ላይ ነበር፤ (16፥8)። የእነርሱን ምሳሌ እንዳንከተል ጳውሎስ አስጠንቅቆናል (1ቆሮ 10፥10 ይመ)።

15፥25 *ወደ ውሃው ጣላት፣ ውሃውም ጣፋጭ ሆነ፤* 2ነገ 2፥19-22 ይመ። *ሕግና ሥርዐት ፤* እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሰጠ ውን መመሪያ የሚያመለክቱ ሲያሚዎች ሲሆኑ ከቍ26 በኋላ የተሰጡ ትን ትእዛዞች ያመለክታሉ። *ፈተናቸው፤* የዘፍ 22፥1 ማብ ይመ። እግዚአብሔር መናን ሲያወርድላቸውና (16፥4፤ዘዳ 8፥2-3 ይመ) ዐሥ ርቱን ትእዛዛት ሲሰጣቸው ፈትኖአቸዋል፤ (20፥20 ይመ)።

15፥27 *ኤሊም፤* ከአይን ሃዋራ 11.26 ኪሎ ሜትር ርቆና (የቍ23 ማብ ይመ)በቂ ውሃ ባለው በጋራዴል ሸለቆ የሚገኝ ስፍራ ነው። *የዘንባባ ዛፎች፤* ኤሊም ማለት "ረጃጅም ዛፎች" ማለት ነው።

16፥1 *ከኤሊም ... ሲን ምድረ በዳ፤* 33፥10-11 ይመ። የሲን ምድረ በዳ የሚገኘው ከሲና ተራራ በስተ ደቡብ ምዕራብ በኩል ሲሆን (ሲን የሚለው ቃል የተገኘው "ሲና" ከሚለው ቃል ነው)፤ በአሁኑ ጊዜ ዴቤቴር ራምሌ ተብሎ በሚጠራው ክልል ውስጥ ነው። *በሁለተኛው ወር በዐሥራ አምስተኛው ቀን፤* እስራ ኤላውያን ከግብፅ ከወጡ አሁን ልክ አንድ ወር ሆኖአቸዋል፤ (12፥2:6:29:31 ይመ)።

16፥2 *አጕረመረሙ፤* የ15፥24 ማብ ይመ።

16፥3 *ሥጋ፤* እስራኤላውያን ከግብፅ ሲወጡ ይዘው የወጡት የምግብ ዐይነት በዘኍ 11፥5 ላይ ተጠቅሶአል።

16፥4 *ከሰማይ እንጀራ፤* ኢየሱስ ስለ ራሱ ሲናገር እንዲህ ብሎ ነበር፣ "ከሰማይ የወረደ እንጀራ" እኔ ነኝ፤ (ዮሐ 6፥32)፤ "የእግዚአብሔር እንጀራ" እኔ ነኝ (ዮሐ 6፥33)፤ "የሕይወት እን ጀራ" እኔ ነኝ፤ (ዮሐ 6፥35:48)፤ "ከሰማይ የወረደ ሕያው እንጀራ" እኔ ነኝ (ዮሐ 6፥51)፤ እነዚህ ቃላት በዚህ ቦታ የገቡት መንፈ ሳዊ ትርጕም ይዘው ነው (ዮሐ 6፥63)። ተመሳሳይ ለሆነ አገባብ

ቸውን ይሰብስቡ፤ በዚህም ትእዛዛቴን ይጠብቁ እንደ ሆነ እፈትናቸዋለሁ:: 5በስድስተኛው ቀን በሌሎቹ ዕለታት ከሚሰበስቡት እጥፍ ሰብስበው ያዘጋጁ::

6ስለዚህ ሙሴና አሮን ለእስራኤላውያን ሁሉ፣ እንዲህ አሉ፤ “ከግብፅ ምድር ያወጣችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ) መሆኑን በዛሬይቱ ምሽት ታውቃላችሁ:: 7በእርሱ ላይ ያሰማችሁትን ማጕረምረም ሰምቷልና በማለዳ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ክብር ታያላችሁ፤ ለመሆኑ በእኛስ ላይ የምታጕረመርሙት እኛ ምንድን ነንና ነው?” አሏቸው:: 8ሙሴም ንግግሩን በመቀጠል፣ “በእርሱ ላይ ማጕረምረማችሁን ሰምቶአልና በምሽት የምትበሉትን ሥጋ፣ በማለዳም የምትፈልጉትን ያህል እንጀራ በሚሰጣችሁ ጊዜ እግዚአብሔር (ያህዌ) መሆኑን ታውቃላችሁ፤ እኛ ማን ነን? በእኛ ላይ አይደለም ያጕረመረማችሁት፤ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ላይ ነው እንጂ” አላቸው::

9ከዚያም ሙሴ አሮንን፣ “ ‘ማጕረምረማችሁን እርሱ ሰምቶአልና ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ቅረቡ’ ብለህ ለመላው የእስራኤል ማኅበር ተናገር” አለው::

10አሮንም ለመላው የእስራኤል ማኅበር ሲናገር ሳለ ወደ ምድረ በዳው ተመለከቱ፤ በዚያም የእግዚአብሔር (ያህዌ) ክብር በደመናው ላይ ተገልጦ ይታይ ነበር::

11እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ 12“የእስራኤላውያንን ማጕረምረም ሰምቻለሁ፤ ይህን ንገራቸው፤ ‘ፀሓይ ከመጥለቋ በፊት ሥጋ ትበላላችሁ፤ ሲነጋም እንጀራ ትበላላችሁ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር አምላካችሁ (ያህዌ ኤሎሂም) መሆኔን ታውቃላችሁ::’ ”

13በዚያች ምሽት ድርጭቶች መጥተው ሰፈሩን አለበሱት፤ በንጋውም በሰፈሩ ዙሪያ ጤዛ ተኝቶበት ነበር:: 14ጤዛው ከረገፈ በኋላ በሜዳው ላይ ስስ የሆነ አመዳይ የሚመስል የተጋገረ ነገር በምድረ በዳው ላይ ታየ:: 15እስራኤላውያንም ይህን ባዩ ጊዜ ምን እንደ ሆነ ባለማወቃቸው እርስ በርሳቸው፣ “ይህ ነገር ምንድን ነው?” ተባባሉ::

ሙሴም፦ “ይህ ትበሉት ዘንድ እግዚአብሔር (ያህዌ) የሰጣችሁ እንጀራ ነው አላቸው:: 16እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘው ይህ ነው፤ ‘እያንዳንዱ የሚያስፈልገውን ያህል ይሰብስብ፤ በድንኳናችሁ ባለው ሰው ልክ ለእያንዳንዱ አንድ ጎሞር[ጣ] ውሰዱ’ ” ብሎ እግዚአብሔር (ያህዌ) አዞአል::

17እስራኤላውያንም እንደ ተነገራቸው አደረጉ፤ አንዳንዶች አብዝተው፣ አንዳንዶች ደግሞ አሳንሰው ሰበሰቡ:: 18የሰበሰቡትን በጎሞር በሰፈሩ ጊዜ ብዙ የሰበሰበው አልተረፈውም፤ ጥቂት የሰበሰበውም አልጐደለበትም፤ እያንዳንዱ የሰበሰበው የሚያስፈልገውን ያህል ሆነ::

19ሙሴም፣ “ማንም ከዚህ ለነገ ምንም ማስተረፍ የለበትም” አላቸው::

20ሆኖም ግን አንዳንዶቹ ሙሴ የተናገረውን ቸል በማለት ከሰበሰቡት ውስጥ ከፊሉን አስተርፈው አሳደሩ፤ በማግሥቱም ጠዋት ተልቶ መሽተት ጀመረ፤ ስለዚህ ሙሴ ተቈጣቸው::

21በየማለዳው እያንዳንዱ የሚያስፈልገውን ያህል ሰበሰበ፤ ፀሓዩ እየበረታ በሄደም ጊዜ ቀለጠ:: 22ስድስተኛው ቀን ለእያንዳንዱ ሰው ሁለት ሁለት ጎሞር[ጨ] አድርገው እጥፍ ሰበሰቡ፤ የማኅበሩም አለቆች ወደ ሙሴ መጥተው ይህንኑ ነገሩት:: 23እርሱም አላቸው፤ “እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘው ይህ ነው፤ ‘ነገ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የተቀደሰ ሰንበት በመሆኑ፣ የዕረፍት ቀን ይሆናል:: ስለዚህ መጋገር የምትፈልጉትን ጋግሩ፤ መቀቀል የምትፈልጉትን ቀቅሉ:: የተረፈውን አስቀምጡ፤ እስከ ጧትም ድረስ አቆዩት::

24ስለዚህ ሙሴ እንዳዘዘው እስከ ጧት ድረስ አቆዩት፤ አልሸተተም፤ ወይም አልተላም:: 25ሙሴም እንዲህ አለ፤ “ዛሬውኑ ብሉት፤ ዛሬ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ሰንበት ነውና:: ዛሬ በመሬት ላይ ምንም አታገኙም:: 26ስድስት ቀን ትሰበስቡታላችሁ፤ በሰባተኛው ቀን በሰንበት ዕለት ግን ምንም ነገር አይኖርም::”

27ሆኖም አንዳንዶቹ በሰባተኛው ቀን ለመሰብሰብ ወጡ፤ ነገር ግን ምንም አላገኙም:: 28ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ ትእዛዞቼንና መመሪያዎቼን ለመፈ

16፥5 ቍ22፤ ዘሌ25፥21
16፥6 ዘፀ6፥6
16፥7 ቍ10:12፤ ዘፀ24፥16፤29፥43፤ 33፥18:22፤40፥34፤ ዘሌ9፥6፤ዘኍ11፥1: 18፤14፥2:27:28፤ 16፥11:19:42፤ 17፥5፤ዘዳ5፥24፤ 1ነገ8፥11፤መዝ63፥2፤ ኢሳ6፥3፤35፥2፤ 40፥5፤44፥23፤60፥1፤ 66፥18፤ሕዝ1፥28፤ 10፥4፤43፥5፤ ዕን2፥14፤ሐጌ2፥7፤ ዮሐ11፥40፤
16፥8 ቍ7፤ ዘኍ23፥21፤ዘዳ33፥5 መሳ8፥23፤ 1ሳሙ8፥7፤12፥12፤ ማቴ10፥40፤ ሮሜ13፥2፤1ተሰ4፥8
16፥10 ቍ7፤ ዘፀ13፥21፤ 40፥34-35፤ 1ነገ8፥10፤2ዜና7፥1፤ ሕዝ10፥4፤ዮሐ11፥4
16፥12 ቍ7፤ ዘፀ6፥2፤20፥2
16፥13 ዘኍ11፥9: 31፤መዝ78፥27-28፤ 105፥40፤106፥15
16፥14 ቍ31፤ ዘኍ11፥7-9፤ ዘዳ8፥3:16፤ መዝ105፥40
16፥15 ቍ4፤ ዘዳ8፥16፤ነህ9፥20፤ ዮሐ6፥31
16፥16 ቍ32:36
16፥18 2ቆሮ8፥15
16፥19 ቍ23፤ ዘፀ12፥10
16፥20 ቍ24፤ ዘፀ32፥19
16፥22 ቍ5፤ ዘፀ34፥31
16፥23 ዘፍ2፥3፤ ዘፀ20፥8፤ዘዳ5፥13-14
16፥26 ቍ23
16፥28 ኢሱ9፥14፤ መዝ78፥10፤ 106፥13፤107፥11፤ 119፥1፤ኤር32፥23

[ጣ]16 ይህ በቍጥር 18:32:33 እንዲሁም 36 ላይ ተጠቅሶአል፤ ወደ ሁለት ሊትር ያህል ይሆናል::
[ጨ]22 ምናልባት ወደ 4.5 ሊትር ሊደርስ ይችላል::

ዘዳ8፥3 ይመ፤ ኢየሱስ ይህንን ቃል በማቴ4፥4 ላይ ጠቅሶታል:: *በየቀኑ እየወጡ ለዕለት የሚበቃቸውን ይሰበስቡ፤* ኢየሱስ በማቴ 6፥11፤ሉቃ11፥3 ላይ ለተናገረው ነገር መሠረት ሳይሆን አይቀርም:: *እፈትናቸዋለሁ፤* የ15፥25 እና የዘፍ 22፥1 ማብ ይመ::

16፥5 *በስድስተኛው ቀን በሌሎቹ ዕለታት የሚሰበስቡትን እጥፍ ሰብስበው ያዘጋጁ፤* እንዲህ የሚያደርጉት “የዕረፍት ቀን” (ቍ 23) በሆነው “በሰባተኛው ቀን” (ቍ 26) ምግብ እንዲሆናቸው ነው:: ቍ 29 ይመ::

16፥6 *ታውቃላችሁ፤* የ6፥3 ማብ ይመ::

16፥8 *በምሽት ... ሥጋ በማለዳም ... እንጀራ፤* ቍ 13-14 ይመ::

16፥10 *የእግዚአብሔር ክብር በደመናው ይታይ ነበር፤* 24፥15-17 ይመ:: እንዲሁም የ13፥21 ማብ ይመ::

16፥12 *ፀሓይ ከመጥለቋ በፊት፤* የ12፥6 ማብ ይመ::

16፥13 *ድርጭቶች ... ሰፈሩን አለበሱት፤* ተመሳሳይ የሆነ ነገር በዘኍ 11፥31-33 ላይ ተጠቅሶ ይገኛል::

16፥14 *ስስ የሆነ ነገር፤* የዘኍ 11፥7 ማብ ይመ::

16፥15 *ይህ ነገር ምንድን ነው?* ቍ 31 ይመ፤ “መና” ማለት “ምንድን ነው” ማለት ነው::

*16፥18፤* 2ቆሮ 8፥15 ይመ፤ ጳውሎስ የዚህን ቍጥር ዋና ሐሳብ ጠቅሶ ያላቸውን ሁሉ እርስ በርሳቸው ይካፈሉ ከነበሩ ክርስቲያኖች ጋር አያይዞታል::

16፥23 *ሰንበት፤* ምንም እንኳ ሰባተኛው ቀን የዕረፍትና የተቀደሰ ቀን እንደ ሆነ በሥነ ፍጥረት ታሪክ ላይ ቢገለጽም ቃሉን ለመጀመሪያ ጊዜ የምናገኘው እዚህ ላይ ነው፤ (የዘፍ 2፥3 ማብ ይመ)::

ጾም እስከ መቼ እምቢ ትላላችሁ[a]? [29]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሰንበትን የሰጣችሁ መሆኑን ልብ በሉ፤ በስድስተኛው ቀን ለሁለት ቀን የሚሆን እንጀራ የሰጣችሁ ለዚህ ነው። በሰባተኛው ቀን እያንዳንዱ ሰው ባለበት ይቆይ፤ ማንም አይወጣም።" [30]ስለዚህ ሕዝቡ በሰባተኛው ቀን ዐረፉ።

[31]የእስራኤልም ሕዝብ ምግቡን መና አሉት[a]፤ እርሱም እንደ ድንብላል ዘር ነጭ፣ ጣሙም ከማር እንደ ተጋገረ እንጀራ ነበር። [32]ሙሴም አለ፤ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘን ይህ ነው፤ 'ከግብፅ ባወጣኋችሁ ጊዜ በምድረ በዳ እንድትበሉ የሰጠኋችሁን ቂጣ ያዩ ዘንድ አንድ ጎሞር መና ወስደህ ለሚመጡት ትውልዶች አቆየው።' "

[33]ስለዚህ ሙሴ አሮንን፣ "አንድ ማሰሮ ወስደህ አንድ ጎሞር መና አስቀምጥበት፤ ለሚመጡት ትውልዶች እንዲቆይም በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት አስቀምጠው" አለው።

[34]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው፣ አሮን መናው ይጠበቅ ዘንድ በምስክሩ ፊት አስቀመጠው። [35]እስራኤላውያን ወደ መኖሪያቸው ምድር እስኪመጡ ድረስ ለአርባ ዓመት መና በሉ፤ ወደ ከነዓን ድንበር እስከሚደርሱ ድረስ መና በሉ።

[36]አንድ ጎሞር የኢፍ መስፈሪያ አንድ ዐሥረኛ ነው።

## ከዐለት የፈለቀ ውሃ

**17** መላው የእስራኤል ማኅበር ከሲና ምድረ በዳ ተነስቶ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘው ከስፍራ ወደ ስፍራ ተጓዞ በራፊዲም ሰፈረ፤ ነገር ግን ሕዝቡ የሚጠጡት ውሃ አልነበረም። [2]ስለዚህ፣ "የምንጠጣው ውሃ ስጠን" በማለት ሙሴን ተጣሉት።

ሙሴም፣ "እኔን ለምን ትጣሉኛላችሁ? እግዚአብሔርንስ (ያህዌ) ለምን ትፈታተኑታላችሁ?" አለ።

[3]ነገር ግን ሕዝቡ በዚያ ተጠምተው ስለ ነበር፣ በሙሴ ላይ አጕረመረሙ። እነርሱም፣ "እኛና ልጆቻችን እንዲሁም ከብቶቻችን በውሃ ጥም እንድናልቅ፣ ከግብፅ ለምን አወጣኸን?" አሉት።

[4]ከዚያም ሙሴ "በዚህ ሕዝብ ምን ላድርግ? በድንጋይ ሊወግሩኝ ተዘጋጅተዋል" ብሎ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጮኸ።

[5]እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ እንዲህ መለሰለት፤ "ከሕዝቡ ፊት ሂድ፤ ከእስራኤል አለቆች አንዳንዶቹን እንዲሁም ዐባይን የመታህባትን በትር ያዝና ሂድ። [6]ኮሬብ አጠገብ ባለው ዐለት በዚያ እኔ በአንተ ፊት እቆማለሁ። ዐለቱን ምታው፤ ከእርሱም ሕዝቡ የሚጠጡት ውሃ ይወጣል።" ስለዚህ ሙሴ በእስራኤል አለቆች ፊት ይህንኑ አደረገ። [7]ስፍራውንም ማሳህና[b] መሪባ[c] ብሎ ጠራው፤ እስራኤላውያን ጠብ ፈጥረው፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) ከእኛ ጋር ነው ወይስ አይደለም" በማለት እግዚአብሔርን (ያህዌ) ተፈታትነዋልና።

## አማሌቃውያን ተሸነፉ

[8]አማሌቃውያን መጥተው እስራኤላውያንን ራፊዲም ላይ ወጉ፤ [9]ሙሴም ኢያሱን፣ "ከሰዎቻችን አንዳንዶቹን ምረጥና አማሌቃውያንን ለመውጋት ውጣ፤ በነገው ዕለት የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም) በትር በእጆቼ ይዤ በኰረብታው ጫፍ ላይ እቆማለሁ።"

16፥31 ቍ14
16፥33 ዕብ9፥4፤ ራእ2፥17
16፥34 ዘፀ25፥16፡21፡22፤27፥21፤31፥18፤40፥20፤ዘሌ16፥13፤ዘኍ1፥50፤17፥8፤9፤10፥11፤17፥4፡10፤ዘዳ10፥2፤1ነገ8፥9፤2ዜና5፥10
16፥35 ዘኍ14፥33፤33፥38፤ዘዳ1፥3፤2፥7፤8፥2-4፤ኢያ5፥6፡12፤ነህ9፥21፤መዝ95፥10፤አሞ5፥25፤ዮሐ6፥31፡49
16፥36 ቍ16፤ ዘሌ5፥11፤6፥20፤ ዘኍ5፥15፤15፥4፤28፥5
17፥1 ቍ8፤ ዘፀ16፥1፤19፥2፤ ዘኍ33፥15፤20፥5፤21፥5፤33፥14
17፥2 ዘፀ14፥12፤ ዘኍ20፥2፤33፥14፤ ዘዳ6፥16፤መዝ78፥18፡41፤106፥14፤107፥5፤ማቴ4፥7፤1ቆሮ10፥9
17፥3 ዘፀ14፥11፤15፥22፡24
17፥4 ዘኍ14፥10፤1ሳሙ30፥6፤ዮሐ8፥59
17፥5 ዘፀ4፥2፤10፥12-13፤7፥20
17፥6 ዘፀ3፥1፤ ዘኍ20፥8፡11፤ዘዳ8፥15፤መሳ15፥9፤2ነገ3፥20፤ነህ9፥15፤መዝ74፥15፤78፥15-16፤105፥41፤107፥35፤114፥8፤ኢሳ30፥25፤35፥6፤43፥19፤48፥21፤1ቆሮ10፥4
17፥7 ዘዳ6፥16፤9፥22፤33፥8፤ ዘኍ20፥13፡24፤27፥14፤መዝ81፥7፤95፥8፤106፥32
17፥8 ቍ1፤ዘፍ36፥12
17፥9 ዘፀ4፥17፤24፥13፤32፥17፤33፥11፤ዘኍ11፥28፤27፥22፤ዘዳ1፥38፤ኢያ1፥1፤ሐሥ7፥45

[a]28 ዕብራይስጡ የብዙ ቍጥር ያሳያል።
[a]31 መና ማለት፣ ምንድን ነው? ማለት ነው (ቍ 15 ይመ)።
[b]7 ማሳህ ማለት መፈተን ማለት ነው።
[c]7 መሪባ ማለት መጣላት ማለት ነው።

*16፥29፤* የቍ 5 ማብ ይመ።

16፥31 *መና፤* የዘኍ 11፥7 ማብ ይመ።

16፥33 *ማሰሮ፤* ይህ ዕቃ የሚሠራው ከወርቅ እንደ ሆነ በዕብ 9፥4 ላይ ተነግሮአል።

16፥34 *በምስክሩ፤* ዐሥርቱ ትእዛዛት የያዙት ጽላቶች "ሁለቱ የምስክር ጽላቶች" ተብለው ተጠርተዋል (31፥18፤32፥15፤ 34፥29)፤ ሁለቱን ጽላቶችና (25፥16፡21 ይመ) መና የሚቀመጥበትን መሶብ (ዕብ 9፥4 ይመ፤ እንዲሁም ራእ 2፥17 እና ማብ ይመ) የሚይዘው ታቦት "የምስክሩ ታቦት" ወይም ታቦተ ሕጉ (25፥22፤26፥33) የሚለውን መጠሪያ ያገኘው ከዚህ ነው።

16፥35 *አርባ ዓመት መና በሉ ... ከነዓን ድንበር እስከሚደርሱ ድረስ መና በሉ፤* መና ከሰማይ መውረዱን ያቆመው እስራኤላውያን ከነዓን ገብተው የመጀመሪያውን የፋሲካ በዓል ሲያከብሩ ነው፤ (ኢያ 5፥10-12 ይመ)።

17፥1 *ከስፍራ ወደ ስፍራ በመዘዋወር፤* የቦታዎቹን ዝርዝር በተመለከተ፣ ዘኍ 33፥12-14 ይመ። *በራፊዲምም፤* ምናልባት ከሲና በስተደቡብ በያቤል ሙሳ (የ3፥1 ማብ ይመ) አቅራቢያ የሚገኘውን ዋዲ ሬፋይድ ወይም ዋዲ ፌራን ሳይሆን አይቀርም።

17፥2 *እግዚአብሔርን ትፈታተናላችሁ፤* እስራኤል እግዚአብሔርን በመፈታተ እግዚአብሔርን ፈተና ወደቀች፤ (16፥4 ይመ)።

17፥3 *አጕረመረሙ፤* የ15፥24 ማብ ይመ።

17፥4 *በዚህ ሕዝብ፤* በእንዲህ ያለ ሁኔታ ውስጥ መራራቅ ሊኖር እንደሚችል፣ ("ሕዝቤ" በማለት ፈንታ "ይህ ሕዝብ") በነቢያት መጻሕፍት ውስጥ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል፤ (ኢሳ 6፥9፤ ሐጌ 1፥2 ይመ)።

17፥6 *ዐለት ... እቆማለሁ፤* ጳውሎስ "ይከተላቸው ከነበረው ከመንፈሳዊ ዐለት" በማለት ስለ ክርስቶስ ሲጽፍ፣ ይህን እያሰበ ሳይሆን አይቀርም፤ (1ቆሮ 10፥4 ይመ፤ እንዲሁም ዕብ 11፥24-26 ይመ)። *በኮሬብ፤* የ3፥1 ማብ ይመ። *ዐለቱን ምታው ... ውሃ ... ይወጣል፤* የእስራኤል መዘምራን ነቢያት ይህን እያስታወሱ ምስጋና አቅርበዋል፤ (መዝ78፥15-16፡20፤ 105፥41፤ 114፥8፤ ኢሳ 48፥21 ይመ)።

17፥7 *ማሳህ ... መሪባ፤* ዕብ 3፥7-8፡15 (ከመዝ 95፥7-8 ላይ የተጠቀሰ ቃል ነው)፤ ማሳህ ማለት "ፈተና" ማለት ነው፤ መሪባ ማለት ደግሞ "ዐመፅ" ማለት ነው ይላል። በቃዴስ በርኔ አቅራቢያ ሌላ መሪባ ተፈጽሞ እንደ ነበር (የዘፍ 14፥7 ማብ ይመ) በዘኍ 20፥13፡24፤ 27፥14፤ ዘዳ 32፥51፤33፥8፤ መዝ 81፥7፤ 106፥32፤ ሕዝ 47፥19፤ 48፥28 ላይ ተገልጾአል።

17፥8 *አማሌቃውያን፤* የዘፍ 14፥7 ማብ ይመ።

17፥9 *ኢያሱን፤* ለነዌ ልጅ ለሆሴዕ ኢያሱ የሚል ስም ያወጣለት ሙሴ ነው፤ (ዘኍ 13፥16 ይመ)። "ሆሴዕ" ማለት "ደኅንነት" ማለት ሲሆን "ኢያሱ" ማለት ደግሞ "እግዚአብሔር ያድናል" ማለት ነው። ኢያሱ ከኤፍሬም ነገድ (ዘኍ 13፥8) የወጣ ሰው ሲሆን ይህ ነገድ ከዐሥራ ሁለቱ ነገዶች ሁሉ በጣም ኀያል ነገድ ነው። *አማሌቃውያንን ለመውጋት፤* ኢያሱ የነበረው ወታደራዊ ብቃትና ችሎታ ከ40 ዓመታት በኋላ ከነዓንን ድል ለማድረግ ሲያስችለው፣ በእግዚአብሔር ላይ የነበረው እምነትና ለሙሴ ያሳየው ታማኝነት የሙሴ "ረዳትና" (24፥13፤33፥11) ምትክ (ዘዳ 1፥38፤ 3፥28፤ 31፥14፤ 34፥9፤ ኢያ 1፥5 ይመ) እንዲሆን አድርጎታል።

[10]ስለዚህ ኢያሱ ሙሴ ባዘዘው መሠረት ከአማሌቃውያን ጋር ተዋጋ፤ ሙሴ፣ አሮንና ሖርም ወደ ኰረብታው ጫፍ ወጡ። [11]ሙሴ እጆቹን ወደ ላይ በሚያነሣበት ጊዜ ሁሉ እስራኤላውያን ድል ያደርጉ ነበር። እጆቹን ባወረደ ጊዜ ግን አማሌቃውያን ያሸንፉ ነበር። [12]የሙሴ እጆች እየዛሉ በሄዱ ጊዜ ድንጋይ ወስደው ከበታቹ አደረጉ፤ እርሱም ተቀመጠበት፤ አሮንና ሖርም አንዱ በአንዱ በኩል ሌላውም በሌላ በኩል ሆነው እጆቹን ወደ ላይ ያዙ። ይኸውም እጆቹ ፀሓይ እስክትጠልቅ ድረስ ጸንተው እንዲቆዩ ነው። [13]ስለዚህ ኢያሱ የአማሌቃውያንን ሰራዊት በሰይፍ ድል አደረገ።

[14]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "ሲታወስ እንዲኖር ይህን በጥቅልል መጽሐፍ ላይ ጻፈው፤ ኢያሱም መስማቱን አረጋግጥ፤ ምክንያቱም የአማሌቃውያንን ዝክር ከሰማይ በታች ፈፅሜ እደመስሳለሁ" አለው።

[15]ሙሴም መሠዊያውን ሠርቶ፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) አርማዬ ነው" ብሎ ሰየመው። [16]"እጆች ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ዙፋን ተዘርግተዋልና፤[T] እግዚአብሔር (ያህዌ) አማሌቃውያንን ከትውልድ እስከ ትውልድ ይዋጋቸዋል" አለ።

## ዮቶር ወደ ሙሴ መጣ

**18** የምድያም ካህን የሙሴ አማት ዮቶር፣ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ለሙሴና ለሕዝቡ ለእስራኤል ያደረገላቸውን ሁሉ እንዲሁም እግዚአብሔር (ያህዌ) እስራኤልን ከግብፅ እንዴት እንዳወጣቸው ሰማ።

[2]ሙሴ ሚስቱን ሲፓራን ከመለሳት በኋላ አማቱ ዮቶር እርሷንና ሁለት ወንድ ልጆቿን ተቀብሏቸው ነበር። [3]ሙሴ፣ "በባዕድ አገር መጻተኛ ነኝ" ለማለት የመጀመሪያ ልጁን ስም ጌርሳም[ሀ] አለው። [4]"የአባቴ አምላክ ረዳቴ ነው፤ ከፈርዖን ሰይፍ አድኖኛልና" ለማለት ደግሞ ሁለተኛውን ልጁን አልዓዛር[ለ] አለው።

[5]የሙሴ አማት ዮቶር ከሙሴ ወንድ ልጆችና ሚስት ጋር ሆኖ በምድረ በዳ ከእግዚአብሔር ተራራ አጠገብ ወደ ሰፈረበት ወደ ሙሴ መጣ። [6]ዮቶር፣ "እኔ አማትህ ዮቶር፣ ከሚስትህና ከሁለት ወንዶች ልጆቿ ጋር እየመጣን ነው" ሲል መልእክት ላከበት።

[7]ስለዚህ ሙሴ አማቱን ሊቀበለው ወጣ፤ ዝቅ ብሎ እጅ በመንሣትም ሳመው፤ ከዚያም ሰላምታ ተለዋውጠው ወደ ድንኳኑ ገቡ። [8]ሙሴም እግዚአብሔር (ያህዌ) ለእስራኤል ሲል በፈርዖንና በግብፃውያን ላይ ያደረገውን ሁሉ፣ በመንገድም ላይ ስላጋጠማቸው መከራ ሁሉና እግዚአብሔርም (ያህዌ) እንዴት እንዳዳናቸው ለአማቱ ነገረው። [9]ዮቶርም እግዚአብሔር (ያህዌ) እነርሱን ከግብፃውያን እጅ በመታደግ ለእስራኤል ያደረገውን በጎ ነገር ሁሉ በመስማቱ ተደሰተ። [10]እንዲህም አለ፤ "ከግብፃውያን እጅና ከፈርዖን ለታደጋችሁ፣ ከግብፃውያን እጅ ሕዝቡን ለታደገ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ምስጋና ይሁን"። [11]"እግዚአብሔር (ያህዌ) ከአማልክት ሁሉ በላይ ኀያል እንደ ሆነ አሁን ዐወቅሁ፤ እስራኤልን በትዕቢት ይዘው በነበሩት ሁሉ ላይ ይህን አድርጎአልና።" [12]ከዚያም የሙሴ አማት ዮቶር የሚቃጠል መሥዋዕትና ሌሎች መሥዋዕቶች ለእግዚአብሔር (ኤሎሂም) አቀረበ፤ አሮንም ከሙሴ አማት ጋር በእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ፊት እንጀራ ለመብላት ከእስ

[T]16 ወይም፣ ምክንያቱም እጅ በእግዚአብሔር ዙፋን ላይ ተዘርግቶአል ... ተብሎ ሊተረጐም ይችላል።
[ሀ]3 በዕብራይስጥ ጌርሳም የሚለው የቃል ድምፅ፣ መጻተኛ በዚያ አለ ከሚለው ሐረግ ጋር ተመሳሳይ ድምፅ አለው።
[ለ]4 አልዓዛር ማለት፣ አምላኬ ረዳት ነው ማለት ነው።

17፥10 ቍ10-12፤ዘፀ24፥14፤31፥2
17፥11 ያዕ5፥16
17፥12 ኢሱ8፥26
17፥13 ቍ8
17፥14 ቍ13፤ ዘኍ36፥12፤ዘፀ24፥4፤ 32፥33፤34፥27፤ ዘኍ24፥7፤33፥2፤ ዘዳ29፥20፤31፥9፤ መሳ3፥13፤1ሳሙ30፥17-18፤ኢዮ18፥17፤ 19፥23፤መዝ9፥5፤ 34፥16፤83፥7፤109፥15፤ሕዝ18፥4፤ ኢሳ30፥8፤ኤር36፥2፤ 45፥1፤51፥60
17፥15 ዘፍ8፥20፤ 22፥14
17፥16 ዘኍ24፥7፤ 1ሳሙ15፥8:32፤ 1ዜና4፥43፤አስ3፥1፤ 8፥3፤9፥5:24
18፥1 ዘፀ2፥16፤ 2፥18፤6፥6
18፥2 ዘፀ2፥21
18፥3 ዘፀ2፥22፤ 4፥20፤ሐሥ7፥29
18፥4 ዘፍ49፥25፤ ዘዳ33፥29፤1ዜና23፥15
18፥5 ዘፀ3፥1
18፥7 ዘፍ17፥3፤ 29፥13፤43፥28
18፥8 ዘፀ15፥6:16፤ ዘኍ20፥14፤ነህ9፥32፤ መዝ81፥7
18፥9 ኢሱ21፥45፤ 1ነገ8፥66፤ነህ9፥25፤ መዝ145፥7፤ ኢሳ63፥7
18፥10 ዘፍ9፥26፤ 24፥27
18፥11 ዘፀ1፥10፤ 12፥12፤1ዜና16፥25፤ ሉቃ1፥51
18፥12 ዘፍ31፥54፤ 26፥30፤ዘፀ3፥1፤ 10፥25፤20፥24፤ 24፥5፤ዘሌ1፥2-9፤ ዘዳ12፥7

17፥10 *ሖርም፤* ምናልባት የካሌብ ልጅና የባስልኤል ቅድመ አያት የሆነው ሖር ነው (1ዜና 2፥19-20 ይመ)፤ ሖር የመገናኛውን ድንኳን ለመሥራት ከተመረጡት ሰዎች መካከል አንዱ ነው (31፥2-5 ይመ)።

17፥11 *እጆቹን ... በሚያነሣበት፤* የእግዚአብሔርን ርዳታና ኀይል መፈለጉን የሚያሳይ ምልክት ነው፤ (የ9፥29 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 9፥22 10፥12፤ 14፥16 ይመ)።

17፥14 *ጻፈው፤* 24፥4፤ 34፥27-28፤ ዘኍ 33፥2፤ ዘዳ 28፥58፤ 29፥20:21:27፤ 30፥10፤ 31፥9:19:22:24 ይመ፤ እንዲሁም በመጽሐፉ መግቢያ ላይ "ጸሓፊውና መጽሐፉ የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ። *በጥቅልል መጽሐፍ፤* ከብራና ወይም ከፓፒረስ (ከመቃ) ቅጠል የሚዘጋጅ ረጅም መጻፊያ ሲሆን፣ ጸሐፍት በዚህ መጻፊያ ላይ በብዕር (ኢሳ 8፥1 ይመ) ወይም በቀለም (ኤር 36፥18 ይመ) ይጽፉታል፤ ጸሐፍቱ በመጻፊያው ላይ የሚጽፉት በዐምድ ከፍለው ሲሆን፤ (ኤር 36፥23) አንዳንድ ጊዜ በፊትና በጀርባ ይጽፉበታል፤ (ሕዝ 2፥10፤ ራእ 5፥1 ይመ)። ጥቅልሉ መጻፊያ ከተጠቀለለ በኋላ፣ መልእክቱ ወይም በጥቅልሉ ላይ የተጻፈው ቃል እንዲጠበቅ በማኅተም ይታተማል፤ (ኢሳ 29፥11፤ ዳን 12፥4፤ ራእ 5፥1-2: 5:9 ይመ)። ጥቅልል መጻፊያዎች የተለያየ ርዝመት/ ቍመት አላቸው፤ (ኢሳ 8፥1፤ራእ10፥2:9-10 ይመ)። በግብፅ የተገኙ ጥቅልል መጻፊያዎች ቁመታቸው (ርዝመታቸው) እስከ 30.46 ሜትር ይደርሳል፤ የመጽሐፍ ቅዱስ ጸሓፊዎች የጻፉበት ጥቅልል ቍመቱ ከ9.14 ሜትር ብዙም አይበልጥም፤ ለምሳሌ ትንቢተ ኢሳይያስ የተጻፈበት ጥቅልል ቁመቱ ወደዚህ አካባቢ ይደርሳል (ሉቃ 4፥17 ይመ)። በጥቅል መጻፊያ ላይ የተጻፉ ነገሮችን የሚያነብ ሰው በአንድ እጁ ጥቅልሉን እየፈታ በአንዱ ደግሞ መጠቅለል አለበት፤ (ኢሳ 34፥4፤ ሕዝ 2፥10፤ ሉቃ 4፥17:20፤ ራእ 6፥14 ይመ)። ከኢየሱስ ዘመን በኋላ ጥቅልል መጻፊያዎች በመጽሐፍ መልክ ተተኩ፤ እስከ አሁን ድረስ የምንጠቀመው በዚህ ዐይነት ነው።

17፥15 *አርማዬ፤* ሙሴ እጁን ወደ ሰማይ ዘርግቶ የለመነውን ልመናና፣ (ቍ11-12:16 ይመ) እግዚአብሔር ሕዝቡን ለመታደግ ሲል የገለጠውን ብርቱ ኀይል የሚያስታውስ ቃል ነው።

18፥1 *የምድያም ካህን ... ዮቶር፤* የ2፥16 ማብ ይመ።

18፥2 *ከመለሳት በኋላ፤* ሙሴ ሲፓራን ወደ አባቷ ወደ ዮቶር ሳይልካት አልቀረም፤ የላካትም እግዚአብሔር ተልዕኮውን እንደባረከለትና (ቍ1 ይመ)፤ አሁን በሲና ተራራ አቅራቢያ ከእስራኤል ሕዝብ ጋር እንደሚገኝ፣ ለዮቶር እንድትነግርለት ነው።

18፥5 *ከእግዚአብሔር ተራራ፤* 3፥1 እና ማብ ይመ።

18፥11 *እግዚአብሔር ከአማልክት ሁሉ በላይ ኀያል እንደ ሆነ አሁን ዐወቅሁ፤* ንዕማን ተመሳሳይ የሆነ ቃል እንደ ተናገረ በ2ነገ 5፥15 ላይ ይመ።

18፥12 *አቀረበ፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ግሥ ለመሥዋዕት የሚሆን እንስሳ "አዘጋጀ" ማለት ነው፤ (25፥2፤ ዘሌ 12፥8 ይመ)። *እንጀራ ሊበሉ፤* ወዳጅነትን የሚገልጽ ነው፤ (ከአማሌቃውያን ጋር የተደረገውን ውጊያ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ 17፥8-16)። በዚህ ዐይነት ምግብ አብረው የበሉ ሰዎች ቃል ኪዳን ይጋባሉ፤ (ዘፍ 31፥54፤ ዘፀ 24፥11 ይመ)።

ራኤል አለቆች ሁሉ ጋር መጣ።

[13]በማግሥቱ ሙሴ ሕዝቡን ለመዳኘት ተቀመጠ፤ እነርሱም በዙሪያው ከጧት እስከ ማታ ድረስ ቆሙ። [14]አማቱም ሙሴ ለሕዝቡ የሚያደርገውን ሁሉ ባየ ጊዜ፣ "ምን ማድረግህ ነው? እነዚህ ሁሉ ሰዎች ከጧት እስከ ማታ በዙሪያህ ቆመው ሳለ፣ ብቻህን በፍርድ ወንበር ላይ ለምን ትቀመጣለህ?" አለው።

[15]ሙሴም እንዲህ ብሎ መለሰለት፤ "ምክንያቱም ሰዎቹ የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ፈቃድ በመፈለግ ወደ እኔ ይመጣሉ። [16]ክርክር በኖራቸው ቍጥር ጉዳያቸው ወደ እኔ ይመጣል፤ ለግራና ለቀኙ የሚሆነውን እኔ ወስኜ የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ሥርዐትና ሕጎች እነግራቸዋለሁ።"

[17]የሙሴ አማት መልሶ እንዲህ አለው። "የምትሠራው መልካም አይደለም። [18]አንተና ወደ አንተ የሚመጡት እነዚህ ሰዎች የምታደርጉት ነገር ቢኖር ራሳችሁን ማድከም ነው፤ ሥራው ለአንተ ከባድ ሸክም ነው፤ ብቻህን ልትወጣው አትችልም። [19]ምክር እሰጥሃለሁና አሁን እኔን አድምጠኝ፤ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ከአንተ ጋር ይሁን። አንተ በእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ፊት (የሕዝብ ተወካይ መሆን አለብህ)፤ ክርክራቸውን ወደ እርሱ ታቀርባለህ። [20]ሥርዐቶቹንና ሕጎቹን አስተምራቸው፤ እንዴት መኖር እንዳለባቸውና ምን መሥራት እንደሚገባቸው አሳያቸው። [21]ነገር ግን ችሎታ ያላቸውን ሰዎች ከሕዝቡ ሁሉ ምረጥ፤ እነዚህም ሰዎች እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) የሚፈሩ፣ ታማኞችና በማታለል የሚገኘውን ጥቅም የሚጸየፉ ይሁኑ። የሺህ፣ የመቶ፣ የአምሳ፣ የዐሥር፣ አለቃ አድርገህ ሹማቸው። [22]በማንኛውም ጊዜ ሕዝቡን ይዳኙ፤ ቀላሉን ነገር እነርሱ ይወስኑ፤ አስቸጋሪ የሆነውን ጉዳይ ሁሉ ግን ለአንተ እንዲያቀርቡ አድርግ፤ ሥራውን ስለሚያግዙህ ሸክምህ ይቃለላል። [23]አንተ ይህን ብታደርግና እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) ይህንኑ ቢያዝህ፣ ድካምህን መቋቋም ትችላለህ፤ እነዚህም ሰዎች ሁሉ ረክተው ወደ ቤታቸው ይሄዳሉ።

[24]ሙሴ አማቱን ሰማ፤ ያለውንም ሁሉ ፈጸመ። [25]ከእስራኤል መካከል ችሎታ ያላቸውን ሰዎች መረጠና፤ የሕዝብ መሪዎች፣ በሺዎች፣ በመቶዎች፣ በአምሳዎች በዐሥሮች ላይም አለቆች አደረጋቸው። [26]ሁልጊዜም የሕዝብ ዳኞች ሆነው አገለገሉ፤ አስቸጋሪ ጉዳዮችን ወደ ሙሴ አመጡ፤ ቀላል የሆነውን ራሳቸው ወሰኑ። [27]ከዚያም ሙሴ አማቱን በጕዞው ሸኘው፤ ዮቶርም ወደ አገሩ ተመለሰ።

## በሲና ተራራ ላይ

**19** በሶስተኛው ወር እስራኤላውያን ከግብፅ ለቀው በወጡበት በዚያችው ዕለት ወደ ሲና ምድረ በዳ መጡ። [2]ከራፊዲም ከተነሡ በኋላ ወደ ሲና ምድረ በዳ ገቡ፤ እስራኤልም በዚያ በምድረ በዳው በተራራው ፊት ለፊት ሰፈሩ።

[3]ከዚያም ሙሴ ወደ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ወጣ፤ እግዚአብሔርም (ያህዌ) ከተራራው ጠራውና እንዲህ አለው፤ "ለያዕቆብ ቤት የምትለው ለእስራኤልም ሕዝብ የምትናገረው ይህ ነው፤ [4]'በግብፅ ላይ ያደረግሁትን፣ በንስርም ክንፍ ተሸክሜ ወደ ራሴ እንዴት እንዳመጣኋችሁ እናንተ ራሳችሁ አይታችኋል። [5]አሁንም በፍጹም ብትታዘዙኝና ቃል ኪዳኔን ብትጠብቁ እነሆ ከአሕዛብ ሁሉ እናንተ የተወደደ ርስቴ ትሆናላችሁ፤ ምንም እንኳ ምድር ሁሉ የእኔ ብትሆንም፣ [6]እናንተ[a] ለእኔ የመንግሥት ካህናት የተቀደሰ ሕዝብ ትሆናላችሁ፤' ለእስራኤላውያን የምትነግራቸው ቃሎች እነዚህ ናቸው።"

18፥15 ቍ19፤ ዘፍ25፥22
18፥16 ቍ15፤ ዘፀ24፥14፤ ዘሌ24፥12፤ ዘኍ15፥34፤ ዘዳ1፥17፤ 2ዜና19፥7፤ ምሳ24፥23፤ ሚል2፥9
18፥18 ዘኍ11፥11: 14:17፤ ዘዳ1፥9:12
18፥19 ቍ15፤ ዘፀ3፥12፤ ዘኍ27፥5
18፥20 ዘፍ39፥11፤ ዘዳ4፥1:5፤5፥1፤ መዝ119፥12:26:68፤ 143፥8
18፥21 ዘፍ22፥12፤ 47፥6፤ ዘፀ23፥8፤ ዘኍ1፥16፤7፥2፤ 10፥4፤ ዘዳ16፥18:19፤ 1ሳሙ12፥3፤ ዕዝ7፥25፤ መዝ15፥5፤ ምሳ17፥23፤28፥8፤ መክ7፥7፤ ሕዝ18፥8፤ 22፥12፤ ሐሥ6፥3
18፥22 ዘሌ24፥11፤ ዘኍ11፥17፤ ዘዳ1፥9: 17-18፤
18፥25 ዘኍ1፥16፤ 7፥2፤11፥16፤ ዘዳ1፥13-15፤16፥18፤
18፥26 ቍ22፤ ዘዳ1፥17፤16፥18፤ 2ዜና19፥5፤ ዕዝ7፥25፤
18፥27 ዘኍ10፥29-30
19፥1 ዘፀ6፥6፤ ዘኍ1፥1፤3፥14፤ 33፥15
19፥2 ቍ17፤ ዘፀ3፥1፤17፥1፤ ዘዳ5፥2-4
19፥3 ዘፀ3፥4፤ 20፥21፤ 25፥22፤ ሐሥ7፥38
19፥4 ዘዳ29፥2፤ 32፥11፤33፥12፤ ኢሱ24፥7፤ መዝ103፥5፤ ኢሳ31፥5፤40፥31፤ ሕዝ16፥6፤ ኤር4፥13፤ 48፥40፤ ራእ12፥14
19፥5 ዘፍ17፥9፤ ዘፀ3፥1፤8፥1:22፤ 34፥9፤9፥29፤ 15፥26፤ ዘዳ6፥31 መዝ78፥10፤ ኤር7፥23፤1ቆሮ10፥26፤ ቲቶ2፥14
19፥6 ዘፍ18፥19፤ ዘሌ11፥44-45፤ ዘዳ4፥37፤7፥6፤26፥19፤28፥9፤29፥13፤33፥3፤ ኢሳ4፥3፤ 61፥6፤62፥12፤ 66፥21፤ ኤር2፥3፤ አሞ3፥2፤1ጴጥ2፥5፤

[a]5 ወይም ምድር ሁሉ የእኔ ርስት ናት፤ እናንተ ...

18፥15 *የእግዚአብሔርን ፈቃድ በመፈለግ፤* የእግዚአብሔርን ፈቃድ የሚያውቁት ወደ አምልኮ ስፍራ በመሄድ (ዘፍ 25፥22 እና ማብ እንዲሁም ዘኍ 27፥21 ይመ) ወይም ነቢይን በመጠየቅ ነው (1ሳሙ 9፥9 ፤ 1ነገ 22፥8 ይመ)።

18፥16 *የእግዚአብሔርን ሥርዐትና ሕጎች፤* አዲስ የተመሠረተችውን የእስራኤልን ሕዝብ የሚመራና የሚገዛ መለኮታዊ ሕግ፣ ቀስ በቀስ እየተሰባሰበና እየተቀረጸ ለሕዝቡ መሰጠት ሳይጀምር አይቀርም፤ (15፥25-26 እና የዘፍ 26፥5 ማብ ይመ)።

19፥2 *ሲና ምድረ በዳ፤* ከባሕር ሰርጡ በስተ ደቡብ ምሥራቅ በሚገኘው ክልል ውስጥ የሚገኝ ስፍራ ነው፤ (የ3፥1 ማብ ይመ)። የዚህ መጽሐፍ ጸሓፊ፣ ከዚህ በኋላ በዘፀአት መጽሐፍ ውስጥ እንዲሁም በዘሌዋውያንና በዘኍልቁ 1፥1-10፥11 ላይ የተወሱት ኹነቶች በዚህ ስፍራ እንደተፈጸሙ አድርጐ ኹነቶቹን ይተርካል።

19፥3 *ለያዕቆብ ... ለእስራኤልም፤* የ1፥1 ማብ ይመ።

19፥4 *በንስርም ክንፍ ተሸክሜ፤* ወርቃማዋ ሴት ንስር ጫጩቶቿን በክንፏ ተሸክማ እንደምትንከባከብ እግዚአብሔርም ሕዝቡን እንደ እዮት መከባከቡን ይገልጻል።

19፥5 *ብትጠብቁ ... ትሆናላችሁ፤* በሲና ተራራ ላይ በእግዚአብሔርና በእስራኤል መካከል የተደረገው ቃል ኪዳን እግዚአብሔር ከ600 ዓመት በፊት ከአብርሃምና ከዘሮቹ ጋር የገባው ቃል ኪዳን ቅጥያ ነው፤ የአሁኑ ቃል ኪዳን የተመሠረተውም ሆነ የተቆራኘው ከቀድሞው ቃል ኪዳን ጋር ነው፤ (በገጽ 19 ላይ "በብሉይ ኪዳን የሚገኙ ዐበይት ኪዳናት" የሚለውን የጥናት መጽሐፍ ይመ)። ከመለኮት የሚገኘውን በረከት ለመካፈል ታዛዥና ታማኝ ሆኖ መገኘት ያስፈልጋል፤ (የዘፍ 17፥9 ማብ ይመ)። *ኪዳኔን፤* የዘፍ 9፥9 ማብ ይመ። *ከአሕዛብ ሁሉ ... የተወደደ ርስቴ ትሆናላችሁ፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆኑ ቃላት በ1ጴጥ 2፥9 ላይ ለክርስቲያኖች ተነግሮአል፤ ቃላቱም "የተመረጠ ሕዝብ" እና "የእግዚአብሔር ወገን" የሚሉ ናቸው፤ (ዘዳ7፥6፤14፥2፤ 26፥18፤ መዝ 135፥4፤ ሚል 3፥17 ይመ)። *ምድር ሁሉ የእኔ ብትሆንም፤* እግዚአብሔር የምድር ፈጣሪና ባለቤት ነው፤ በምድር ላይ የሚገኘው ነገር ሁሉ የእርሱ ነው (ዘፍ14፥19:22፤ መዝ24፥1-2 ይመ)።

19፥6 *የመንግሥት ካህናት ፤* እስራኤል የእግዚአብሔር መንግሥት መሆን አለባት፤ (የእግዚአብሔርን መንግሥት የተቀበለች ሕዝብ መሆን አለባት)፤ እንዲሁም እንደ ካህን ራሷን ለእግዚአብሔር አገልግሎት ሙሉ በሙሉ መስጠት አለባት፤ (ኢሳ 61፥6 ይመ፤ ከ1ጴጥ 2፥5፤ ከራእ 1፥6፤ 5፥10፤ 20፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። *የተቀደሰ ሕዝብ፤* 1ጴጥ 2፥9 ይመ። የእግዚአብሔር ሕዝብ በኅብረትም ሆነ በግል የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለማድረግ፤ (ዘዳ 7፥6፤ 14፥2:21፤ 26፥19፤ ኢሳ62፥12 ይመ) ራሳቸውን "መለየት" አለባቸው፤ (የ3፥5 ማብ ይመ)።

[7]ስለዚህ ሙሴ ተመልሶ የሕዝቡን አለቆች አስጠራ፤ እንዲናገር እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘውን ቃሎች ሁሉ ነገራቸው። [8]ሕዝቡም ሁሉ በአንድ ላይ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ያለውን ሁሉ እናደርጋለን" ብለው መለሱ፤ ስለዚህ ሙሴ እነርሱ ያሉትን መልሶ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ወሰደ።

[9]እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "ከአንተ ጋር ስናገር ሕዝቡ እንዲሰሙኝና እምነታቸውን ምንጊዜም በአንተ ላይ እንዲጥሉ በከባድ ደመና ወደ አንተ እመጣለሁ" ከዚያም ሙሴ ሕዝቡ ያሉትን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ነገረው።

[10]እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "ወደ ሕዝቡ ሂድና ዛሬና ነገ ቀድሳቸው፤ ልብሳቸውን እንዲያጥቡ አድርግ፤ [11]በሦስተኛውም ቀን ይዘጋጁ፤ ምክንያቱም በዚያ ቀን በሕዝቡ ፊት እግዚአብሔር (ያህዌ) በሲና ተራራ ላይ ይወርዳል። [12]በተራራው ዙሪያ ለሕዝቡ ወሰን አበጅተህ እንዲህ በላቸው፤ 'ወደ ተራራው እንዳትወጡ ወይም ግርጌውን እንዳትነኩ ተጠንቀቁ፤ ማንም ተራራውን ቢነካ በርግጥ ይሞታል። [13]በድንጋይ ይወገራል ወይም በቀስት ይወጋል፤ ምንም እጅ በእርሱ ላይ አያርፍም፤ ሰውም ሆነ እንስሳ በሕይወት እንዲኖር አይተውም።' ወደ ተራራው መውጣት የሚችሉት ከፍ ባለ ድምፅ መለከት በተነፋ ጊዜ ብቻ ነው።"

[14]ሙሴ ከተራራው ወርዶ ወደ ሕዝቡ ከሄደ በኋላ ቀደሳቸው፤ ልብሳቸውንም አጠቡ። [15]ከዚያም ለሕዝቡ፣ "ለሦስተኛው ቀን ራሳችሁን አዘጋጁ፤ የግብረ ሥጋ ግንኙነት ከማድረግ ተቈጠቡ" አላቸው።

[16]በሦስተኛውም ቀን ጧት ከባድ ደመና በተራራው ላይ ሆኖ ነጐድጓድና መብረቅ እንዲሁም ታላቅ የቀንደ መለከት ድምፅ ነበር፤ በሰፈሩ ያሉት ሁሉ ተንቀጠቀጡ። [17]ከዚያም ሙሴ ከእግዚአብሔር (ያህዌ) ጋር ለማገናኘት ሕዝቡን ከሰፈር ይዞ ወጣ፤ ከተራራውም ግርጌ ቆሙ። [18]የሲና ተራራ እግዚአብሔር (ያህዌ) በእሳት ስለ ወረደበት በጢስ ተሸፍኖ ነበር። ጢሱ ከምድጃ እንደሚወጣ ጢስ ወደ ላይ ተትጐለጐለ፤ ተራራውም በሙሉ[ሠ] በኀይል ተናወጠ። [19]የመለከቱም ድምፅ እያየለ መጣ። ከዚያም ሙሴ ተናገረ፤ እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) በድምፅ መለሰለት።[ሠ]

[20]እግዚአብሔር (ያህዌ) በሲና ተራራ ጫፍ ላይ ወረደ፤ ሙሴን ወደ ተራራው ጫፍ ጠራው፤ ሙሴም ወጣ። [21]እግዚአብሔርም (ያህዌ) እንዲህ አለው፤ "ሕዝቡ እግዚአብሔርን (ያህዌ) ለማየት በመጣደፍ ብዙዎቹ እንዳይጠፉ ውረድና አስጠንቅቃቸው [22]ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚቀርቡት ካህናት እንኳ ራሳቸውን መቀደስ አለባቸው፤ አለዚያ እግዚአብሔር (ያህዌ) ቍጣውን ያወርድባቸዋል።"

[23]ሙሴ እግዚአብሔርን (ያህዌ) እንዲህ አለው፤ "ሕዝቡ ወደ ሲና ተራራ ሊወጡ አይችሉም፤ ምክንያቱም አንተ ራስህ 'በተራራው ዙሪያ ወሰን አድርግ፤ የተቀደሰም በማድረግ ለየው' በማለት አስጠንቅቀኸናልና።"

[24]እግዚአብሔርም (ያህዌ) እንዲህ አለ፤ "ውረድና አሮንን ከአንተ ጋር ይዘኸው ውጣ፤ ካህናቱና ሕዝቡ ግን ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ለመምጣት መጣደፍ የለባቸውም፤ አለዚያ እርሱ ቍጣውን ያወርድባቸዋል።"

[25]ስለዚህ ሙሴ ወደ ሕዝቡ ወርዶ ነገራቸው።

## ዐሥርቱ ትእዛዛት

20፥1-17 ተጓ ምብ - ዘዳ 5፥6-21

**20** እግዚአብሔር (ኤሎሂም) እነዚህን ቃሎች ሁሉ እንዲህ ብሎ ተናገረ፤

19፥7 ዘፀ18፥12፤ ዘሌ4፥15፡30፤9፥11፤ ዘኍ16፥25፤ 1ሳሙ8፥10
19፥8 ዘፀ24፥3፡7፤ ዘዳ5፥27፤26፥17
19፥9 ቍ16፤ ዘፀ 4፥5፤20፥21፤24፥15-16፤33፥9፤34፥5፤ዘዳ 4፥11፡12፡36፤2ሳሙ 22፥10፡12፤2ዜና 6፥1፤መዝ18፥11፤ 97፥2፤99፥7፤ማቴ17፥ 5፤ዮሐ12፥29-30፤
19፥10 ቍ14፡22፤ ዘፍ35፥2፤ዘሌ11፥44፤ ዘኍ11፥18፤1ሳሙ 16፥5፤ኢዩ2፥16፤ዕብ 10፥22፤ራእ22፥14
19፥11 ቍ3፡16፡ 20፤ዘፍ11፥5፤ዘፀ 3፥1፤24፥16፤31፥18፤ 34፥2፡4፡29፡32፤ዘሌ 7፥38፤26፥46፤27፥34 ፤ዘኍ3፥1፤ዘዳ10፥5፤ ነህ9፥13ገላ4፥24-25
19፥12 ቍ23
19፥13 ቍ21፤ዘፀ 34፥3፤ኢያ6፥4፤ 1ዜና15፥28፤መዝ81 ፥3፤98፥6፤ዕብ12፥20
19፥14 ዘፍ35፥2
19፥15 1ሳሙ21፥4 ፤1ቆሮ7፥5
19፥16 ቍ9፤ዘፍ 3፥10፤1ሳሙ2፥10፤ 1ሳሙ13፥7፤14፥15፤ 28፥5፤መዝ99፥1ኢሳ 29፥6፤ዕብ12፥18-19 ፡21፤ራእ4፥1
19፥17 ቍ2፤ዘዳ 4፥11
19፥18 ዘፍ19፥28፤ ዘፀ3፥2፤20፥18፤24፥ 17፤ዘሌ9፥24፤ዘዳ4፥ 11፡24፡33፡36፤5፥4፤ 9፥3፤መሳ5፥5፤2ሳሙ 22፥8፤1ነገ18፥24፡38 ፤1ዜና21፥26፤2ዜና 7፥1፤መዝ18፥7፡8፤ 68፥8፤104፥32፤ኢሳ 2፥19 15፥25፤6፥4፤ 41፥15፤64፥1፤ኤር 4፥24፤10፥10፤ሚክ 1፥4፤ናሆ1፥5፤ዕን3፥6 ፡10፤ሐጌ2፥6፤ዕብ12፥ 18፤ራእ9፥2፤15፥8
19፥19 ቍ9፤ ዘዳ4፥33፤ነህ9፥13፤መዝ81፥7 19፥20 ቍ11 19፥21 ቍ13፤ዘፀ 24፥10-11፤ዘኍ4፥20፤1ሳሙ6፥19 19፥22 ቍ24፤ዘሌ10፥3፤1ሳሙ 16፥5፤2ሳሙ6፥7፤2ዜና29፥5፤ኢዩ2፥16፤ 19፥23 ቍ11፡12
19፥24 ቍ22፤ዘፀ24፥1፡9፤ 20፥1 ዘዳ10፥4፤ነህ9፥13፤መዝ119፥9፤ 147፥19፤ሚል4፥4

[ሠ]18 ብዙ የዕብራይስጥ ቅጂዎችና የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም፣ ሕዝቡ ሁሉ ይላሉ።
[ሠ]19 ወይም፣ እግዚአብሔርም በነጐድጓድ መለሰለት ተብሎ ሊተረጐም ይችላል።

19፥8 *እግዚአብሔር ያለውን ሁሉ እናደርጋለን፤* ሕዝቡ የኪዳኑን ቃል ሁሉ ለመፈጸም ቃል ገባ (24፥3፡7፤ ዘዳ 5፥27 ይመ)።

19፥9 *በከባድ ደመና ... እመጣለሁ፤* 13፥21 እና ማብ ይመ። *ከአንተ ጋር ስነጋገር ሕዝቡ እንዲሰሙኝና፤* ዘዳ 4፥33 ይመ። *እምነታቸውን በአንተ ላይ እንዲጥሉ፤* 14፥31 እና ማብ ይመ።

*19፥10-11፤* የውጭ ሰውነትን አንጽቶ እግዚአብሔርን ለመቀበል መዘጋጀት፣ እግዚአብሔር ከሕዝቡ የሚፈልገውን ውስጣዊ ቅድስና ያሳያል።

*19፥12-13፤* እግዚአብሔር በዚያ በመገኘቱ ተራራው በሙሉ ተቀደሰ (3፥5 እና ማብ ይመ)። እስራኤል ከተወሰነው ድንበር አልፋ ወደ መገናኛው ድንኳን ውስጥ መግባት እንደማትችል፤ (ዘኍ 3፥10 ይመ)፤ እንዲሁም አሁን ወደ ተራራው መውጣት አትችልም።

19፥15 *የግብረ ሥጋ ግንኙነት ከማድረግ ተቈጠቡ፤* ይህ ትእዛዝ የተሰጠው የግብረ ሥጋ ግንኙነት ኀጢአት ስለ ሆነ ሳይሆን፣ ሕዝቡ በእግዚአብሔር ፊት ሲቀርብ ሥነ ሥርዐታዊ ርኵሰት እንዳይገኝበት ነው (ዘሌ 15፥18 ይመ፤ እንዲሁም 1ሳሙ 21፥4-5 ይመ)።

19፥16 *ነጐድጓድና መብረቅ ... የቀንደ መለከት ድምፅ፤* የእግዚአብሔር መገለጥ እንዲህ ባሉ ክሥተቶች የታጀበ ነው፤ (1ሳሙ 7፥10፤ 12፥18፤ ኢዮ 38፥1፤ 40፥6፤ መዝ 18፥13-14 ይመ)። *ከባድ ደመና፤* 13፥21 እና ማብ ይመ።

19፥18 *በእሳት ... ጢሱም ከምድጃ እንደሚወጣ፤* ዘፍ 15፥17 እና ማብ ይመ።

19፥22 *ካህናት፤* እንዲሁም ቍ 24 ይመ። በአሮን አማካይነት የክህነት አገልግሎት ከመጀመሩ በፊት፣ (28፥1 ይመ) የክህነት አገልግሎት ይሰጥ የነበረው በሽማግሌዎች (የ3፥16 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 3፥18፤ 12፥21፤ 18፥12 ይመ)፤ ወይም በወጣት ወንዶች ነበር፤ (24፥5 ይመ)። ይህ ቍጥር የሚናገረው ወደ ፊት በአሮን አማካይነት ስለሚጀመረው የክህነት አገልግሎት ሳይሆን፣ አይቀርም። *ወደ እግዚአብሔር የሚቀርቡት፤* መሥዋዕት ለማቅረብ ነው፤ (40፥32፤ ዘሌ 21፥23 ይመ)።

*20፥1-17፤* ዘዳ 5፥6-21 ይመ፤ ማቴ 5፥21፡27፡19፥17-19፤ ማር 10፥19፤ ሉቃ 18፥20፤ ሮሜ 13፥9፤ ኤፌ 6፥2-3 ይመ።

20፥1 *ቃሎች፤* በጥንት መካከለኛው ምሥራቃውያን ዘንድ፣ ይህ ቃል "ቃል ኪዳን" የሚለውን አሳብ ለመግለጽ የቆመ መደ

[2]"ከግብፅ ከባርነት ምድር ያወጣሁህ *እግዚአብሔር* ስምላክህ (ያህዌ ኤሎሂም) እኔ ነኝ::
[3]"ከእኔ በቀር[ሩ] ሌሎች አማልክት አይኑሩህ::
[4]"በላይ በሰማይ ወይም በታች በምድር ካለው ወይም በውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች በማናቸውም ምስል ለራስህ ጣዖትን አታብጅ:: [5]አትስገድላቸው፤ አታምልካቸውም፤ እኔ *እግዚአብሔር* ስምላክህ (ያህዌ ኤሎሂም) የሚጠሉኝን ልጆች ከአባቶቻቸው ኀጢአት የተነሣ እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ድረስ የምቀጣ ቀናተኛ ስምላክ (ኤሎሂም) ነኝ፤ [6]ነገር ግን ለሚወዱኝና ትእዛዛቴን ለሚጠብቁ እስከ ሺህ ትውልድ ድረስ ፍቅርን የማሳይ ነኝ::
[7]"*የእግዚአብሔር* (ያህዌ) የአምላክህን ስም ያለ አግባብ አታንሣ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ስሙን ያለ አግባብ የሚያነሣውን በደል አልባ አያደርገውምና::
[8]"የሰንበትን ቀን ቅዱስ አድርገህ አክብር:: [9]ስድስት ቀን ትሠራለህ፤ ሥራህንም ሁሉ አከናውን:: [10]ሰባተኛው ቀን ግን ለአምላክህ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ሰንበት ነው:: በዕለቱ አንተም ሆንህ ወንድ ልጅህ ወይም ሴት ልጅህ፣ ወንድ አገልጋይህ ወይም ሴት አገልጋይህ፣ ወይም እንስሳትህ፣ ወይም በግቢህ ያለ መጻተኛ ምንም ሥራ አትሠሩም:: [11]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሰማ ይንና ምድርን፤ ባሕርንና በውስጡም ያሉ

20፥2 ዘፍ15፥7፤ 17፥7፤ዘፀ6፥6፤13፥3፤ 16፥12፤ዘሌ19፥2፤ 20፥7፤ኢሳ43፥3፤ ሕዝ20፥6:19
20፥3 ቍ23፤ ዘፀ34፥14፤ዘዳ6፥14፤ 13፥10፤2ነገ17፥35፤ መዝ44፥20፤81፥9፤ ኤር1፥16፤7፥6:9፤ 11፥13፤19፥4፤25፥6፤ 35፥15
20፥4 ቍ5:23፤ዘፀ 32፥8፤34፥17፤ዘሌ 19፥4፤26፥1፤ዘዳ 4፥15-19:23፤27፥15 ፤2ሳሙ7፥22፤1ነገ14 ፥9፤2ነገ17፥12ኢሳ 40፥19፤42፥8፤44፥9
20፥5 ዘፍ9፥25፤ዘፀ 23፥13:24፤ 34፥7፤ 34፥14፤ ዘሌ26፥39፤ ዘኍ14፥18፤ ዘዳ 4፥24፤ኢሱ23፥7፤ 24፥19፤መሳ6፥10፤ 2ነገ17፥35፤ኢሳ 44፥15:17:19፤46፥6፤ናሆ1፥2፤ኤር32፥18፤20፥6፤ 20፥6 ዘፀ34፥7፤ ዘኍ14፥18፤ዘዳ7፥9፤ኤር32፥18፤ሉቃ1፥50፤ሮሜ11፥28
20፥7 ዘፀ22፥28፤ዘሌ18፥21፤19፥12፤22፥2፤24፥11:16፤ዘዳ6፥13፤ 10፥20፤ኢዮ2፥5:9፤መዝ63፥11፤ኢሳ8፥21፤ሕዝ20፥39፤39፥7፤ማቴ 5፥33 20፥8 ዘፀ16፥23፤31፥13-16፤35፥3፤ዘሌ19፥3:30፤26፥2፤ኢሳ 56፥2፤ኤር17፥21-27፤ሕዝ22፥8 20፥9 ዘፀ23፥12፤31፥13-17፤ 34፥21፤35፥2-3፤ዘሌ23፥3፤ሉቃ13፥14 20፥10 ዘፍ2፥3፤ዘፀ31፥14፤ ዘሌ23፥38፤ዘኍ28፥9፤ኢሳ56፥2፤ሕዝ 20፥12:20

[ሩ]3 ወይም፣ *ከእኔ ጋር* ተብሎ መተርጐም ይችላል::

በኛ ስያሜ ነው፤ (ቃሉ በሒታውያንም ዘንድ የተለመደ ነው፤ 24፥3:8፤ 34፥28 ይመ):: ለእስራኤል የተሰጣት መለኮታዊ ሕግ ከቍ 2-17 ላይ የተጠቀሰው ሲሆን ይህ መለኮታዊ ሕግ በሌላ ስፍራ "ዐሥርቱ ትእዛዛት" (34፥28፤ ዘዳ 4፥13፤ 10፥4) ተብሎ ተጠቅሶአል:: ይህን ሐረግ ለመግለጽ የገቡት የዕብራይስጥ ቃላት ዐሥርቱ ቃላት" የሚል ፍቺ ያላቸው ሲሆን፣ ከሁለት የግሪክ ቃላት የተገኘው "ዴካሎግ" የሚለው ስያሜ አብዛኛውን ጊዜ ዐሥርቱ ትእዛዛት ከሚለው ሐረግ ጋር ተመሳሳይ ፍቺ ይዞ ይገኛል፤ ዴካሎግ ማለት "ዐሥርቱ ቃላት" ማለት ነው::

20፥2 ... *ያወጣሁህ እግዚአብሔር አምላክህ እኔ ነኝ፤* በመደበኛው አጠራር "ዐሥርቱ ትእዛዛት" ተብለው የሚታወቁት አወቃቀራቸው/በቅርጻቸው በዚያን ዘመን የነበሩ ነገሥታት ሕዝባቸው ጋር የሚያደርጉትን ቃል ኪዳን/ስምምነት ያንጸባርቃል፤ (የዘፍ 15፥7 ማብ ይመ):: በዚያን ዘመን የነበሩ ስምምነቶች አጠቃላይ አወቃቀራቸው የሚከተለውን ይመስላል፤ (1) የቃላት መክፈቻ፤ ይህ ክፍል ታላቁ ንጉሥ የራሱን ማንነት የሚያሳውቅበት ነው ("እግዚአብሔር አምላክህ እኔ ነኝ")፤ (2) ታሪካዊ መግቢያ፤ ይህ ክፍል ታላቁ ንጉሥ ከበታቹ ላሉት ነገሥታትና ሕዝቦች ያደረገላቸውን ቸርነት/በጎነት የሚያሳውቅበት ነው፤ ("ከባርነት ምድር ያወጣሁህ")፤ መሠረት በማድረግ፤ (3) ሕዝቡ የሚታዘዘውን የቃል ኪዳኑን ወይም የስምምነቱን ማሠሪያ ሕጎች አንድ በአንድ ይዘረዝራል፤ (ዘዳ 5፥1-3:7-12 ይመ)፤ በዚህ ክፍል የተዘረዘሩት የቃል ኪዳኑ ወይም የስምምነቱ ማሠሪያ ሕጎች ዐሥር ናቸው፤ (ቍ 3-17):: ይህ የጥንት ነገሥታት የቃል ኪዳን (የስምምነት) የሕግ ንድፍ የሚያሳየው እግዚአብሔር የእስራኤል ንጉሥ እንደ ሆነና እስራኤል ደግሞ የእግዚአብሔር ባሪያ እንደ ሆነች ነው:: እስራኤል የእግዚአብሔር ባሪያ በመሆን የቃል ኪዳኑ ሕዝቦች፣ እግዚአብሔር ካደረገላቸው ምሕረት፣ ለታላቅነቱ ካላቸው አክብሮትና ወደ ፊትም የሚያስፈልጋቸውን ሁሉ እንደሚያዘጋጅላቸው ካላቸው እምነት የተነሣ በፍጹም ልባቸው ሊገዙለት፣ ሊታመኑበትና ሊታዘዙት ይገባል::

20፥3 *ከእኔ በቀር ሌሎች አማልክት፤* በየትኛውም ጊዜና ሰዓት በእስራኤል ልብና ሕይወት ውስጥ ብቸኛውን እውነተኛ አምላክ የሚቀናቀን በእጅ የተጠረበ ወይም በምናብ የተቀረጸ አንድም አምላክ ሊኖር አይገባም::

20፥4 *በማናቸውም ... ምስል፤* እግዚአብሔር በዐይን የሚታይ መልክ ስለሌለው የእርሱን መልክ ለመግለጽ የሚቀረጽ ምስል ሁሉ ኀጢአት ይሆናል (ዘፀ 4፥12:15-18)፤ ሌሎች ማናቸውንም አማልክት ማምለክ ተገቢ ባለመሆኑ (ቍ5) በእነርሱ ምስል ጣዖትን መቅረጽ እንዲሁ ኀጢአት ነው (ዘፀ 4፥19:23-28 ይመ)::

20፥5 *ቀናተኛ አምላክ፤* እግዚአብሔር ተቀናቃኝም ሆነ ከዳተኛ ሆኖ አያውቅም:: አብዛኛውን ጊዜ "ቀናተኛ" የሚለው አነጋገር የሚያመለክተው፣ እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር ያለውን የቃል ኪዳን ግንኙነት (በጋብቻ ውስጥ ካለው ግንኙነት ጋር ተመሳሳይ) ሲሆን፣ እግዚአብሔር ያለ አንዳች ተቀናቃኝ እስራኤልን ጠቅልሎ የመውሰድና ከእስራኤል ፍቅርንና ታማኝነትን የማግኘት መብት እንዳለውም ያሳያል:: እርግጥ "ቀናተኛ" የሚለው ቃል "ፍቅር" ከሚለው ቃል ጋር የትርጕም ዝምድና አለው:: የእግዚአብሔር "ቀናተኛነት" ግን (1) እርሱን ብቻ ማምለክን ይጠይቃል፤ (34፥14፤ ዘዳ 4፥24፤ 32፥16:21፤ኢሱ 24፥19፤ መዝ 78፥58፤ 1ቆሮ 10፥22፤ ያዕ 4፥5 ይመ)፤ (2) እርሱን የሚቃወሙትን ለፍርድ አሳልፎ ይሰጣል (ዘዳ 29፥20፤ 1ነገ 14፥22፤ መዝ 79፥5፤ ኢሳ 42፥13:59፥17፤ ሕዝ 5፥13:16፥38: 23፥25፤ 36፥5፤ ናሆ 1፥2፤ ሶፎ 1፥18:3፥8)፤ (3) የእርሱ ለሆኑ ሕዝቦች ፍትሕን ይሰጣል (2ነገ 19፥31፤ ኢሳ 9፥7: 26፥11፤ ሕዝ 39፥25፤ ኢል 2፥18፤ ዘካ 1፥14:8፥2 ይመ):: ከእነዚህ ክፍሎች በአንዳንዶቹ ውስጥ የቃሉ ፍቺ/ትርጕም "ቅናት" ከሚለው ጋር ተቀራራቢ ነው፤ (ምናልባት ያው አንዱ የዕብራይስጥ ቃል እንደየአጠገባቡ በሁለቱም መልኩ ተተርጕሞ ሊሆን ይችላል):: *የሚጠሉኝን ልጆች እስከ ሦስትና እስከ አራት ትውልድ፤* የእግዚአብሔርን ቃል ኪዳን ሆነ ብለው የሚቃወሙና የእርሱንም ጌትነትና ንጉሥነት የማይቀበሉ እስራኤላውያን በራሳቸውና በቤተ ሰቦቻቸው ላይ ፍርድን ያመጣሉ፤ (ዘኍ 16፥31-34: ኢሱ 7፥24 እና ማብ ይመ):: አብዛኛውን ጊዜ ቤተሰቦች የሚለው ቃል እስከ "ሦስት ወይም እስከ አራት" ትውልድ ድረስ ያሉትን ሁሉ ይጨምራል:: (የመዝ 109፥12 ማብ ይመ):: *በሚጠሉኝ፤* በእግዚአብሔርና በእስራኤል መካከል የተደረገውን ቃል ኪዳን አስመልክቶ በተነገረበት ቦታ ሁሉ፣ "በሚጠሉኝ" እና "ለሚወዱኝ" (ቍ 6) የሚሉት ቃላት የሚያመለክቱት እግዚአብሔርን መቃወም ወይም መታዘዝ ነው::

20፥6 *እስከ ሺህ ትውልድ ድረስ፤* 1ዜና 16፥15፤ መዝ 105፥8 ይመ:: *ለሚወዱኝና ትእዛዛቴን ለሚጠብቁ፤* ዮሐ 14፥15፤ 1ዮሐ 5፥3 ይመ:: በጥንት መካከለኛው ምስራቅ የስምምነት/የቃል ኪዳን ማሠሪያ ሕጎች ውስጥ ለታላቁ ንጉሥ የሚሰጠው፣ "ፍቅር" ታማኝነትን፣ ታዛዥነትና ተገዢነትን የሚገልጽ ነው::

20፥7 *የአምላክህን ስም ያለ አግባብ አታንሣ፤* በረባ ባልረባ የእግዚአብሔርን ስም እየጠራህ አታቃል ማለት ነው፤ ለምሳሌ ለምስክርነት ተጠርተህ ፍርድ ቤት ስትቆም በሐሰት አትማል፤ (ዘሌ 19፥12፤ ኤር 7፥9 ይመ)፤ ክርስቶስ በማቴ 5፥33-37 ላይ መሐላን አስመልክቶ በሰፊው ተናግሮአል::

*20፥8፤* ዘፍ 2፥3 ይመ:: *የሰንበትን፤* የ16፥23ን ማብ ይመ:: *ቅዱስ፤* የ3፥5 ማብ ይመ::

20፥9 *ስድስት ቀን፤* በኢንዱስትሪ በበለጸጉ አገሮች ያለውን አጭር "የሥራ ሳምንት" አስመልክቶ የሚነሳውን ጥያቄ አያመለክትም::

20፥10 *በዕለቱ ... አትሠሩም፤* ትእዛዙን አስመልክቶ ሁለት ምክንያቶች (አንደኛው በዚህ ቦታ ሌላው ደግሞ በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ተጠቅሶአል) ተሰጥተዋል፤ (1) እግዚአብሔር የፍጥረት ሥራውን ከፈጸመ በኋላ "በሰባተኛው ቀን ዐረፈ" (ቍ 11) እንዲሁም እስራኤላውያን በፍጥረት ሥራው እግዚአብሔርን ሲያገለግሉ ይህንኑ መንገድ መከተል ይኖርባቸዋል:: (2) እግዚአብሔር ሕዝቡን ከግብፅ ባርነት ነጻ እንዳወጣ ሁሉ፣ (ዘዳ 5፥14-15 ይመ)፤ እስራኤላውያንም አገልጋዮቻቸው የሰንበትን ዕረፍት እንዲካፈሉ እነርሱም ከማናቸውም ሥራ ማረፍ አለባቸው:: ስለዚህ

ትን ሁሉ በስድስት ቀን ፈጥሮ፤ በሰባተኛው ቀን አርፎአልና:: ስለዚህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሰንበትን ቀን ባረከው፤ ቀደሰውም::

[12] 'አባትህንና እናትህን አክብር፤ *እግዚአብሔር* ስምባክህ (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ ምድር ዕድሜህ እንዲረዝም::

[13]"አትግደል::

[14]"አታመንዝር::

[15]"አትስረቅ::

[16]"በባልንጀራህ ላይ በሐሰት
አትመስክር::

[17]"የባልንጀርህን ቤት አትመኝ፤ የባልንጀራህን ሚስት ወይም የእርሱን ወንድ አገልጋይ ሆነ ሴት አገልጋይ፣ በሬውንም ሆነ አህያውን ወይም የእርሱ የሆነውን ማናቸውንም ነገር አትመኝ::

[18]"ሕዝቡም መብረቁንና ነጎድጓዱን የተራራውን መጤስና የመለከቱን ድምፅ ባዩና በሰሙ ጊዜ በፍርሃት ተንቀጠቀጡ፤ በርቀትም ቆሙ፤ [19]ሙሴን፣ "አንተ ራስህ ተናገረን፤ እኛም እናደምጥሃለን፤ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) እንዲናገረን አታድርግ፤ አለበለዚያ መሞታችን ነው" አሉት::

[20]ሙሴም ለሕዝቡ፣ "አትፍሩ፤ ኀጢአት እንዳትሠሩ የእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ፍርሃት ከእናንተ ጋር ይሆን ዘንድ፣ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ሊፈትናችሁ መጥቶአል" አላቸው::

[21]እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ወዳለበት ጥቅጥቅ ወደ ሆነው ጨለማ ሙሴ ቀርቦ ሳለ፣ ሕዝቡ በርቀት ቆመው ነበር::

## ጣዖቶችና መሠዊያዎች

[22]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ "ለእስራኤላውያን ይህን ንገራቸው፤ 'ከሰማይ ሆኜ እንደ ተናገርኋችሁ እናንተ ራሳችሁ አይታችኋል፤ [23]ከእኔ በቀር ሌሎች አማልክት አይኑሯችሁ፤ ከብር ወይም ከወርቅ ለእናንተ አማልክትን አታብጁ::

[24]" 'የጭቃ መሠዊያን ሥራልኝ፤ በእርሱም ላይ የሚቃጠልና የኅብረት መሥዋዕትን[a] ከበጎችህ፣ ከፍየሎችህና ከቀንድ ከብቶችህ ሠዋልኝ፤ ስሜ እንዲከበር በማደርግበት ቦታ ሁሉ ወደ አንተ እመጣና እባርክሃለሁ:: [25]ከድንጋይ መሠዊያ የምትሠራልኝ ከሆነ፣ ከጥርብ ድንጋይ አትሥራው፤ መሣሪያ የነካው ከሆነ ታረክሰዋለ

20፥11 ዘፍ1፥3-2፥1፤2፥2፤ዘፀ 31፥17፤ዕብ4፥4
20፥12 ዘፍ4፥23፤31፥35፤ዘዳ5፥16፤6፥2፤11፥9፤25፥15፤ኤር35፥7፤20፥13፤ማቴ5፥21፤15፥4፤19፥18፡19፤ማር 7፥10፤10፥19፤ሉቃ 18፥20፤ሮሜ13፥9፤ኤፌ6፥2፡3፤ያዕ2፥11
20፥14 ዘሌ18፥20፤20፥10፤ዘኍ5፥12፡13፡29፤ምሳ6፥29፡32፤ማቴ5፥27፤19፥18፤ማር10፥19፤ሉቃ18፥20፤ሮሜ13፥9፤ያዕ2፥11
20፥15 ዘሌ19፥11፡13፤ሕዝ18፥7፤ማቴ 19፥18፤ማር10፥19፤ሉቃ18፥20፤ሮሜ 13፥9
20፥16 ዘፀ23፥1፡7፤ዘሌ19፥11፡18፤መዝ 50፥20፤101፥5፤119፥29፤ኤር9፥3፡5፤ማቴ 19፥18፤ማር10፥19፤ሉቃ3፥14፤18፥20
20፥17 ሉቃ12፥15፤ሮሜ7፥7፤13፥9፤ኤፌ 5፥3፤ዕብ13፥5
20፥18 ዘፍ 3፥10፤ዘፀ14፥31፤19፥16-19፤ዘዳ4፥36፤ኢሳ58፥1፤ኤር6፥17፤ሕዝ33፥3፤ዕብ12፥18-19፤ራእ1፥10፤
20፥19 ዘዳ5፥5፡23-27፤18፥16፤ኢዮ37፥4፡5፤40፥9፤መዝ29፥3-4፤ገላ3፥19 20፥20 ዘፍ15፥1፤22፥1፤ዘዳ4፥10፤6፥2፡24፤10፥12፤ኢዮ 1፥8፤2፥3፤28፥28፤መዝ111፥10፤128፥1፤ምሳ1፥7፤3፥7፤8፥13፤14፥16፤16፥6፤መክ12፥13፤ኢሳ8፥13 20፥21 ዘፀ19፥9፤ዘዳ5፥22፤መዝ18፥9፤68፥4፤97፥2፤ኢሳ19፥1 20፥22 ዘዳ5፥24፡26፤ነህ9፥13
20፥23 ቍ3፤ዘፀ22፥20፤32፥4፡8፡31፤34፥17፤ዘዳ29፥17-18፤ነህ 9፥18 20፥24 ዘፍ8፥20፤12፥2፤22፥17፤ዘፀ18፥12፤27፥1፡5፤40፥29፤ዘኍ16፥38፤ዘዳ12፥5፤16፥6፡11፤26፥2፤ኢሱ8፥30፤1ነገ9፥3፤2ነገ 16፥14፤21፥4፡7፤2ዜና4፥1፤2ዜና6፥6፤12፥13፤ዕዝ3፥2፤ዕዝ6፥12፤ሕዝ43፥13 20፥25 ኢሱ8፥31፤1ነገ6፥7

[a]24 በትውፊት፣ *የሰላም መሥዋዕት* በመባል ይታወቃል::

ሰንበት በእስራኤልና በእግዚአብሔር መካከል ላለው/ለተደረገው ቃል ኪዳን "ምልክት" ነው፤ (31፥12-17 *ይመ* የዘፍ 9፥12 ማብ *ይመ*)::

20፥12 *አክብር፤* (1) ከፍ ያለ ዋጋ ስጥ፣ (ምሳ 4፥8 *ይመ*) (2) ተንከባከብ፣ (*መዝ* 91፥15 *ይመ*) (3) አክብሮት ስጥ፣ (ዘሌ 19፥3፡20፥9 *ይመ*) (4) *ታዘዝ* (ዘዳ 21፥18-21፤ ከኤፌ 6፥1 ጋር ያነጻጽሩ) ማለት ነው:: *ዕድሜህ እንዲረዝም፤* "የተስፋ ቃል ያለበት የመጀመሪያ ትእዛዝ ነው"፤ (ኤፌ 6፥2፤ ዘዳ 6፥2 እና ማብ *ይመ*)::

*20፥13፤* ማቴ 5፥21 *ይመ*:: *አትግደል፤* ይህን አሳብ ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል አብዛኛውን ጊዜ አስቀድሞ የታሰበና ሆን ተብሎ የተፈጸመን ድርጊት ያመለክታል::

*20፥14፤* ማቴ 5፥27-30 *ይመ*:: *አታመንዝር፤* በእግዚአብሔርና (ዘፍ 39፥9) በትዳር ጓደኛ ላይ የሚፈጸም በደል ነው::

20፥17 *አትመኝ፤* በክፉ ሐሳብ ተይዞ አንድን ነገር መሻት ማለት ነው፤ (ማቴ 15፥19 *ይመ*):: የእግዚአብሔርን ትእዛዛት በልብ/በስውር መተላለፍ በድርጊት/በግልጽ ከመተላለፍ ጋር እኩል ነው፤ (ማቴ 5፥21-30 *ይመ*)::

*20፥18-21፤* ይህ፣ የዐሥርቱን ትእዛዛት መስጠት ታሪክ የሚያጠቃልል ክፍል ነው:: የታሪኩ ቅደም ተከተል ከሁነቱ ቅደም ተከተል የተለየ ይመስላል፤ ምክንያቱም ቍ18፤ የ19፥25 ተከታይ ነው:: በዚህ ክፍል ዐሥርቱ ትእዛዛት ለሕዝቡ የተላለፉት ሙሴ እግዚአብሔር ወዳለበት ሄዶ ከተመለሰ በኋላ ነው፤ (ቍ 21):: የቅዱሳት መጻሕፍት ጸሐፊዎች ከተለያየ የአጻጻፍ ስልት የተነሣ አብዛኛውን ጊዜ በትረካቸው ውስጥ የጊዜ ቅደም ተከተል አይጠብቁም:: በዚህ ቦታ የጊዜ ቅደም ተከተል ያልተጠበቀበት ምክንያት፣ (1) ዐሥርቱን ትእዛዛት "ከቃል ኪዳኑ መጽሐፍ" (24፥7) ለይቶ ለማስቀመጥ (20፥22-23፥19) ወይም (2) ሙሴ የቃል ኪዳኑ አማካይ (መካከለኛ ሰው) አገልጋይ መሆኑን በይፋ ለማወጅ ወይም ሁለቱንም ሊሆን ይችላል::

*20፥19፤* ዕብ 12፥19-20 *ይመ*:: እስራኤላውያን በእነርሱና በእግዚአብሔር መካከል የሚቆም "መካከለኛ ሰው" እንዲሰጣቸው በጠየቁ ጊዜ ሙሴ ተሰጣቸው፤ ከእርሱም በኋላ ካህናት፣ ነቢያትና ነገሥታት በመጨረሻም ኢየሱስ ክርስቶስ ተሰጣቸው::

20፥20 *አትፍሩ፤* እግዚአብሔር ክብሩን የሚገልጸው እኛን በፍርሃት ለማሸበር ነው ብላችሁ አታስቡ፤ እግዚአብሔር በዚህ መልክ የሚገለጠው እርሱን ሰማያዊ ንጉሣችሁ አድርጋችሁ እንድትቀበሉት ከእናንተ ጋር ቃል ኪዳን ለመግባት ነው:: *ሊፈትናችሁ፤* የዘፍ 22፥1 ማብ *ይመ*:: *የእግዚአብሔር ፍርሀት፤* የዘፍ 20፥11 ማብ *ይመ*::

*20፥22-23፥19፤* "በኪዳኑ መጽሐፍ" (24፥7) ላይ የተጠቀሱት ሕጎች በአብዛኛው ዐሥርቱን ትእዛዛት የሚያስፋፉና የሚያብራሩ ናቸው::

*20፥22-26፤* ይህ ክፍል እስራኤል ከእግዚአብሔር ጋር ሊኖራት የሚገባውን ግንኙነት ምን መልክ መያዝ እንዳለበት የሚገልጸውን የመጀመሪያ ትእዛዝ የያዘ ነው:: (ከቍ 3 ጋር ያነጻጽሩ)::

20፥22 *ከሰማይ፤* የእግዚአብሔር መኖሪያና ማደሪያ ነው:: "እግዚአብሔር በሲና ተራራ ጫፍ ላይ ወርዶ" (19፥20) ከሰማይ የተናገረበት ጊዜም ነበር::

*20፥23* ቍ 3-4 *ይመ*:: "በሰማይ" በሚኖረውና "ደስ የሚያሰኘውን ሁሉ ማድረግ" በሚችለው፣ (*መዝ* 115፥3) ብቸኛው እውነተኛ አምላክና ከቶ ምንም ማድረግ በማይችሉት (*መዝ* 115፥4-7፤ እንዲሁም *መዝ* 135፥5-6፡15-17 *ይመ*)፤ የብርና የወርቅ ጣዖታት መካከል ያለው ንጽጽርና ልዩነት በእርግጥም እጅግ የሚያስገርም ነው::

20፥24 *የጭቃ መሠዊያ፤* በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከሚገኙት መሠዊያዎች ጋር (27፥1 *ይመ*)፣ ተመሳሳይ ስፍረ ርዝመት ያለው የጭቃ መሠዊያ ማለትም በብረት ዘመን (በ10ኛው ወይም በ11ኛው ክፍለ ዘመን ከክርስቶስ ልደት በፊት)፣ ከፓለስታየን በስተ ደቡብ አራድ ተብሎ በሚጠራው ስፍራ በሚገኝ አንድ አነስተኛ የእስራኤላውያን ቤተ መቅደስ ፍርስራሽ ሥር ተገኝቶአል:: *የሚቃጠል መሥዋዕት፤* የዘሌ 1፥3 ማብ *ይመ*:: *የኅብረት መሥዋዕት፤* የዘሌ 3፥1 ማብ *ይመ*:: *በማደርግበት ቦታ ሁሉ፤* ከጊዜ በኋላ በኢየሩሳሌም በታነጸው ቤተ መቅደስ ውስጥ ሳይሆን በሌሎች ጊዜያዊ የአምልኮ ስፍራዎች ማለት ነው፤ (ኢሱ 8፥30-31፤ *መሳ* 6፥24፡21፥4፤ 1ሳሙ 7፥17፡ 14፥35፤ 2ሳሙ 24፥25፤ 1ነገ 18፥30 *ይመ*)::

20፥25 *ከድንጋይ መሠዊያ የምትሠራልኝ ከሆነ፣ በጥርብ ድንጋይ አትሥራ፤* ከጥርብ ድንጋይ ያልተሠሩ በርካታ ጥንታዊ መሠዊያዎች በመካከለኛው ምሥራቅ ተገኝተዋል:: *መሣሪያ የነካው ከሆነ ታረክሱታላችሁ፤* ምክንያቱ ምን እንደ ሆነ ባይታወቅም መሣሪያ እንዳይነካው የተከለከለው ከአረማውያን ልምድ

ህና:: [26]ወደ መሠዊያዬም በደረጃ አት ውጣ፤ አለዚያ ኀፍረተ ሥጋህ ይገለጣል'::

# 21

"በፊታቸው የምትደነግጋቸው ሥርዐቶች እነዚህ ናቸው፤

## ዕብራዊ አገልጋይ

21፥2-6 ተዓ ምብ - ዘዳ 15፥12-18፤ 21፥2-11 ማመ - ዘሌ 25 39-55

[2]"ዕብራዊ አገልጋይ ብትገዛ ስድስት ዓመት ያገልግልህ፤ በሰባተኛው ዓመት ግን ያለምንም ክፍያ በነጻ ይሂድ:: [3]ብቻውን መጥቶ ከሆነ፣ ብቻውን በነጻ ይሂድ፤ ነገር ግን ሲመጣ ባለ ሚስት ከሆነ፣ እርሷ አብራው ትሂድ:: [4]ጌታው ሚስት አጋብቶት ወንድ ወይም ሴት ልጅ ከወለደችለት፣ ሴትዮዋና ልጆቿ የጌታቸው ይሆናሉ፤ ሰውዬው ብቻ በነጻ ይሂድ::

[5]"ነገር ግን አገልጋዩ፤ 'ጌታዬን፤ ሚስቴንና ልጆቼን እወዳለሁ ነጻ ሆኜ አልሄድም' ቢል፣ [6]ጌታው ወደ ዳኞች[ª] ይውሰደው፤ ወደ በር ወይም ወደ በሩ መቃን ወስዶ ጆሮውን በወስፌ ይብሳው፤ ከዚያም ዕድሜ ዘመኑን የእርሱ አገልጋይ ይሆናል::

[7]"አንድ ሰው ሴት ልጁን አገልጋይ እንድትሆን ቢሸጣት፣ እንደ ወንዶቹ አገልጋዮች በነጻ መሸኘት የለባትም:: [8]ለእርሱ ትሆነው ዘንድ የመረጣትን ጌታዋን ደስ ባታሰኘው፣[+] በዎጆ ይስደዳት፤ ለባዕዳን ይሸጣት ዘንድ መብት የለውም፤ ምክንያቱም ለእርሷ ያለውን ታማኝነት አጓድሏልና:: [9]ለወንድ ልጁ ትሆን ዘንድ መርጧት ከሆነ እንደ ራሱ ልጅ የሚገባትን መብት ይስጣት:: [10]ሌላ ሴት ቢያገባ፣ ለመጀመሪያ ሚስቱ ምግቧን፣ ልብሷንና የጋብቻ መብቷን አይከልክላት:: [11]እነዚህን ሦስት ነገሮች የማያሟላላት ቢሆን፣ ያላንዳች የገንዘብ ክፍያ በነጻ መሄድ ይኖርባታል::

## በሕይወት ላይ ለሚደርስ ጉዳት

[12]"ሰውን ደብድቦ የገደለ ሞት ይገባዋል:: [13]ሆኖም እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ፈቅዶ ሰውየው ሳያውቅ በድንገት አድርጎት ከሆነ፣ እኔ ወደምወስነው ስፍራ ይሽሽ:: [14]አንድ ሰው በተንኰል ሆን ብሎ ሌላውን ቢገድል፣ ከመሠዊያዬ ተወስዶ ይገደል::

[15]"አባቱን ወይንም እናቱን የሚመታ[ª] ይገደል::

[16]"አንዱ ሌላውን ጠልፎ የሸጠ ወይም በተያዘ ጊዜ ከእጁ ላይ የተገኘበት ይገደል::

[17]"አባቱን ወይንም እናቱን የሚሰድብ ይገደል::

[18]ሰዎች ተጣልተው አንዱ ሌላውን በድንጋይ ወይም በቡጢ[+] ቢመታውና ተመቺው ሳይሞት በአልጋ ላይ ቢውል፣ [19]በትሩንም ይዞ ደጅ ለደጅ የሚል ቢሆን፣ በዱላ የመታው ሰው አይጠየቅበትም፤ ሆኖም ለተጐጂው ሰው ለባከነበት ጊዜ ገንዘብ ይክፈል፤ ፈጽሞ እስኪድን ክትትል ያድርግለት::

[20]"አንድ ሰው ወንድ ወይም ሴት ባሪያውን በዱላ ቢመታና ባሪያውም በዚህ የተነሣ ቢሞት መቀጣት አለበት፤ [21]ነገር ግን ከአንድ ወይም ከሁለት ቀን በኋላ ባሪያው ቢነሣ መቀጣት የለበትም፤ ባሪያው ንብረቱ ነውና::

[22]"በጥል ላይ ያሉ ሰዎች ነፍሰ ጡር ሴት ቢመቱና እርሷም ያለጊዜዋ ብትወልድ፣[*] ጉዳቱም ለከፋ የማይሰጥ ቢሆን፣ ጉዳት ያደረሰባት ሰው የሴትዮዋ ባል የጠየቀውንና ፈራጆቹ የፈቀዱትን ካሣ ሁሉ መክፈል አለበት:: [23]ነገር ግን የከፋ ጉዳት ቢደርስ ሕይወት በሕይወት፣ [24]ዐይን በዐይን፤

20፥26 ሕዝ43፥17
21፥1 ዘፀ24፥3፤ 34፥32፤ዘዳ4፥14፤6፥1
21፥2 ቍ7፤ዘፀ 22፥3፤ኤር34፥8:14
21፥5 ዘዳ15፥16
21፥6 ዘፀ22፥8-9፤ ዘዳ17፥9፤19፥17፤ 25፥1፤ኢዮ39፥9፤ 41፥4፤መዝ40፥6
21፥10 1ቆሮ7፥3-5
21፥12 ቍ15:17፤ ዘፍ4፥14:23፤ ዘፀ31፥15፤ዘሌ20፥9: 10፤24፥16፤27፥29፤ ዘኍ1፥51፤35፥16: 30-31፤ዘዳ13፥5፤ 19፥11፤22፥22፤ 27፥16፤ኢዮ31፥11፤ ምሳ20፥20፤ ማቴ26፥52
21፥13 ዘኍ35፥ 10-34፤ ዘዳ4፥42፤ 19፥2-13፤ኢሱ20፥9
21፥14 ዘፍ4፥8፤ ዘኍ35፥20፤ዘዳ19፥ 11-12፤1ነገ2፥28-34፤ 2ሳሙ3፥27፤ 20፥10፤ዕብ10፥26፤
21፥16 ዘፍ37፥28፤ ዘፀ22፥4፤ዘዳ24፥7
21፥17 ቍ12፤ ዘዳ5፥16፤ማቴ15፥4፤ ማር7፥10
21፥21 ዘሌ25፥44-46
21፥22 ቍ30
21፥23 ዘሌ24፥19፤ ዘዳ19፥21 21፥24 ቍ23፤ማቴ5፥38

[ª]6 ወይም፣ ወደ ፈራጆች
[+]8 ወይም፣ ጌታዋ ይሆን ዘንድ አይምረጣት
[ª]15 ወይም፣ የሚገድል
[+]18 ወይም፣ በዕቃ
[*]22 ወይም፣ ቢያስወርዳት

(ከሥርዐተ አምልኮአቸው) ጋር በተያያዘ መልክ ሳይሆን አይቀርም::

20፥26 *በደረጃ፤* በመካከለኛው ምስራቅ እጅግ ጥንታዊ የሆነውና ደረጃ ወይም የመወጣጫ መሰላል ያለው መሠዊያ በመጊዶ የተገኘ ሲሆን፣ ዘመኑም ዓ.ቅ.ክ. ከ3000-2500 ዓመት ዓለም ይሆናል:: *ኀፍረተ ሥጋህ ይገለጣል፤* ደረጃ ባለው መሠዊያ ላይ እየወጡ የሚያገለግሉ ካህናት ኀፍረተ ሥጋቸውን በእግዚአብሔር ፊት ሊያራቁቱ ይችላሉ:: አሮንና ዘሮቹ ደረጃ ባለው መሠዊያ ላይ ቢያገለግሉም፣ (ዘሌ 9፥22፤ ሕዝ 43፥17 ይመ)፣ ኀፍረተ ሥጋቸው እንዳይታይ/እንዳይገለጥ ከጥሩ በፍታ የተሠራ የውስጥ ሱሪ እንዲለብሱ ታዘው ነበር፤ (28፥42-43፤ ዘሌ 6፥10: 16፥3-4፤ ሕዝ 44፥17-18 ይመ)::

*21፥2-11፤* ኤር 34፥8-22 ይመ::

21፥2 *ዕብራዊ፤* የዘፍ 14፥13 ማብ ይመ:: *በሰባተኛው ዓመት ... በነፃ ይሂድ፤* የእግዚአብሔር አገልጋዮች ዕድሜአቸውን ሙሉ፣ (ዕድሜ ልካቸውን) የማንም ባሪያ ሆነው መቅረት የለባቸውም፤ (20፥10 እና ማብ ይመ)::

21፥6 *ዳኞች፤* 22፥8-9:28:: *ጆሮውን በወስፌ ይብሳው፤* ዘዳ 15፥17 ይመ:: ለእንደዚህ ዓይነቱ ሥርዓት ራስን ማስገዛት በሙሉ ፈቃደኝነት ለማገልገል መነሣትን ያመለክታል፤ (መዝ 40፥6-8 እና የመዝ 40፥6 ማብ ይመ)::

*21፥12-15፤* 20፥13 እና ማብ ይመ፤ ዘኍ 35፥16-34፤ ዘዳ 19:1-13:21፥1-2፤ 24፥7: 27፥24-25፤ ኢሱ 20፥1-9 ይመ::

*21፥12፤* ዘፍ 9፥6 እና ማብ ይመ::

21፥13 *ሰውየው ሳያውቅ በድንገት፤* ይህ አሳብ በሌሎች ቦታዎች ተዛማጅ በሆኑ ቃላት ተገልጾአል፤ ለምሳሌ "በስሕተት" ዘኍ35፥11፣ "በድንገት" ዘኍ35፥22፣ "ጠላቱም ባይሆን" ዘኍ 35፥23፣ "ክፉም ያደርግበት ዘንድ ባይሻ" ዘኍ 35፥23፣ "ሳያስብ" ዘዳ 19፥4፣ ስለዚህ ሆን ብሎ መግደልና ድንገት መግደል እጅግ የተለያዩ ነገሮች ናቸው:: *እግዚአብሔር ፈቅዶ፤* ከሰው አቅም በላይ የሆነን ድርጊት የሚያመለክት ሲሆን፣ በዘመናዊ የሕግ ቋንቋ "እግዚአብሔር እንዲሆን የወደደው" ማለት ነው:: *ስፍራ፤* የመማፀኛ ከተማ ተብለው የሚታወቁትን ነው፤ (ዘኍ 35፥6-32፤ ዘዳ 19፥1-13፤ኢሱ 20፥1-9:21፥13:212: 27:32:38 ይመ)::

21፥14 *ከመሠዊያዬ ተወስዶ፤* ከሕግ በታች ለሆኑ ሰዎች የመጨረሻ መማፀኛ ናቸው፤ (1ነገ 1፥50-51: 2፥28፤ አሞ 3፥14 እና ማብ ይመ::

*21፥15፤* 20፥12 ይመ::

*21፥16፤* 20፥15 ይመ::

21፥19 *በትሩን ይዞ ደጅ ለደጅ የሚል ቢሆን፤* ቢያገግምና ተሽሎት ቢታይ ለማለት ነው:: *ላባከነበት ጊዜ፤* ቃል በቃል ሲተረጉም "ያለ አንዳች ሥራ ቢቀመጥ" ማለትም ወደ ሳይሆን በግዱ ሥራ ቢፈታ ማለት ነው::

*21፥20-21፤* አንድ ባሪያ አሳዳሪ ባሪያውን ሆን ብሎ መግደሉን የሚያረጋግጥ ምንም ማስረጃ ከሌለ፣ ባሪያ አሳዳሪው ነጻ እንደሚሆን የሚናገር ክፍል ነው::

*21፥23-25፤* ዘፀ 19፥21 ይመ:: በዚህ ዐውደ ንባብ ውስጥ

ጥርስ በጥርስ፣ እጅ በእጅ፣ እግር በግር፣ ¹⁵ቃጠሎ በቃጠሎ፣ ቍስል በቍስል፣ ግር ፋት በግርፋት ታስከፍላለህ::

[26]"አንድ ሰው የወንድ ወይም የሴት አገልጋዩን ዐይን መትቶ ቢያጠፋ፣ ስለ ዐይን ካሣ አገልጋዩን ነጻ ይልቀቀው:: [27]የወንድ ወይም የሴት አገልጋዩን ጥርስ ቢሰብር፣ ስለ ጥርስ ካሣ አገልጋዩን ነጻ ይልቀቀው::

[28]"በሬ አንድን ወንድ ወይም ሴት ወግቶ ቢገድል፣ በሬው በድንጋይ ተወግሮ ይሙት፤ ሥጋውም አይበላ፤ ነገር ግን የበሬው ባለ ቤት በኀላፊነት አይጠየቅም:: [29]ሆኖም በሬው የመውጋት ዐመል ያለበት ሆኖ ለባለ ቤቱም ማስጠንቀቂያ ተሰጥቶት ሳለ በበረት ሳያስ ቀረው ቀርቶ አንድን ወንድ ወይም ሴት ቢገድል፣ በሬው በድንጋይ ይወገር፤ ባለቤቱም እንዲሁ ተወግሮ ይሙት:: [30]ሆኖም ካሣ እንዲከፍል ከተጠየቀ፣ የተጠየቀውን ሁሉ በመክፈል ሕይወቱን ይዋጅ:: [31]አንድ በሬ አንድን ወንድ ወይም ሴት ልጅ ቢወጋ በዚሁ ሕግ መሠረት ይፈጸም:: [32]አንድ በሬ ወንድ ወይም ሴት ባሪያን ቢወጋ ባለቤቱ ሠላሳ የብር ሰቅል[ሀ] ለባሪያው ጌታ መክፈል አለበት፤ በሬውም በድንጋይ ይወገር::

[33]"አንድ ሰው ጕድጓድን ከፍቶ ቢተው፣ ወይም ጕድጓድ ቆፍሮ ሳይከድነው ቢቀርና በሬ ወይም አህያ ቢገባበት፣ [34]የጕድጓዱ ባለቤት ኪሳራ ይክፈል፤ ለባለቤቱ መክፈል አለበት፤ የሞተውም እንስሳ ለእርሱ ይሆናል::

[35]"የአንድ ሰው በሬ የሌላውን ሰው በሬ ወግቶ ቢገድለው፣ በሕይወት ያለውን በሬ ሸጠው ገንዘቡንና የሞተውን እንስሳ እኩል ይካፈሉ:: [36]ሆኖም በሬው የመዋጋት ዐመል ያለው መሆኑ ከታወቀ፣ ባለ ቤቱም በረት ሳይዘጋበት ቢቀር፣ ባለቤቱ በሬውን በበ ሬው ፈንታ ይክፈል፤ የሞተውም እንስሳ ለእርሱ ይሆናል::

### ንብረትን ስለ መጠበቅ

**22** "አንድ ሰው በሬ ወይም በግ ሰርቆ ቢያርድ ወይም ቢሸጥ በአንድ በሬ ምትክ አምስት በሬዎች፤ በአንድ በግ ምትክ አራት በጎች ይክፈል::

[2]"አንድ ሌባ በር ሲሰብር ተይዞ ቢደበ ደብና ቢሞት፣ ተከላካዩ የደም ባለ ዕዳ አይሆንም፤ [3]ነገር ግን ፀሓይ ከወጣች በኋላ ከተፈጸመ፣[ለ] ሰውየው በነፍስ ግድያ ይጠ የቃል::

"ሌባ የሰረቀውን መክፈል አለበት፤ ምንም ከሌለው ግን የሰረቀውን ይከፍል ዘንድ ይሸጥ::

[4]"የሰረቀው እንስሳ በሬ ወይም አህያ፣ ወይም በግ ከነ ሕይወቱ በእጁ ከተያዘ እጥፍ መክፈል አለበት::

[5]"አንድ ሰው ከብቶቹን በመስክ ወይም በወይን ቦታ አሰማርቶ እንዲሁ ስድ ቢለቃ ቸውና የሌላውን ሰው መስክ ቢግጡ፣ ምርጥ ከሆነው ከራሱ መስክ ወይም የወይን ቦታ መክፈል አለበት::

[6]"እሳት ተነሥቶ ወደ ቍጥቋጦ ቢዛም ትና ክምርን ወይም ያልታጨደን እህል ወይም አዝመራውን እንዳለ ቢበላ፣ እሳቱን ያቀጣጠለው ሰው ካሣ ይክፈል::

[7]"አንድ ሰው ብሩ ወይም ንብረቱ ያለሥ ጋት ይጠበቅለት ዘንድ ለጎረቤቱ ሰጥቶ ሳለ ቢሰረቅበትና፣ ሌባው ቢያዝ እጥፍ ይክ ፈል፤ [8]ሌባው ካልተያዘ ግን፣ የቤቱ ባለቤት በንብረቱ ስርቆት ላይ እጁ ይኑር በት ወይም አይኑርበት ይታወቅ ዘንድ ዳኞች ፊት[ሐ] ይቅረብ:: [9]አንድ ሰው በሬን፣ አህያን፣ በግን፣ ልብስን፣ ወይም ማናቸው ንም ንብረት ያለ አግባብ በባለቤትነት ይዞ ሳለ፣ 'የኔ ነው' ባይ ቢመጣና ክርክር ቢነሣ፣ ባለ ጉዳዮቹ ነገሩን ለዳኞች ያቅር ቡት፤ ዳኞቹ ጥፋተኛ ነው ያሉትም[መ] ለጎረ ቤቱ እጥፉን ይክፈል::

[10]"አንድ ሰው አህያ፣ በሬ፣ በግ፣ ወይም ማናቸውንም እንስሳ በጎረቤቱ ዘንድ በአደራ አስቀምጦ ሳለ እንስሳው ቢሞት፣ ወይም ጉዳት ቢደርስበት፣ ወይም ሰው ሳያይ ተነድቶ ቢወሰድ፣ [11]በሁለቱ መካከል ያለው አለመግባባት መፍትሂ የሚያገኘው፣ ጎረቤቱ

21፥28 ቍ32፤ ዘፍ9፥5
21፥29 ቍ36
21፥30 ቍ22
21፥32 ዘፍ37፥28፤ ዘካ11፥12-13፤ማቴ 26፥15፤27፥3፡9
21፥33 ሉቃ14፥5
21፥36 ቍ29
22፥1 ዘሌ6፥1-7፤ 2ሳሙ12፥6፤ምሳ6፥31፤ሉቃ19፥8
22፥2 ዘኍ35፥27፤ ኢዮ24፥16፤ ኤር2፥34፤ሆሴ7፥1፤ ማቴ6፥19-20፤ 24፥43፤
22፥3 ቍ1፤ ዘፀ21፥2፤ማቴ18፥25
22፥4 ዘፍ43፥12፤ 1ሳሙ12፥5
22፥5 ቍ1
22፥6 ቍ1፤ መሳ15፥5
22፥7 ቍ10፤ ዘፍ43፥12፤ዘሌ6፥2
22፥8 ዘፀ21፥6
22፥9 ቍ8፤ ዘዳ25፥1
22፥10 ቍ7
22፥11 ዘሌ6፥3፤ 1ነገ8፥31፤2ዜና6፥22 ዕብ6፥16

[ሀ]32 ወደ 0.3 ኪሎ ግራም ይደርሳል
[ለ]3 ወይም፣ *ከመታው* ተብሎ መተርጐም ይችላል::
[ሐ]8 በዚህም ሆነ በቍጥር 9 ላይ ያለው፣ *እግዚአብሔር ፊት* ተብሎ መተርጐም ይችላል::
[መ]9 ወይም፣ *እግዚዘብሔር ጥፋተኛ ነው ያለውም* ተብሎ መተርጐም ይችላል::

እንደሚታየው በተለምዶ የበቀል ሕግ የሚባለው ለተፈጸመው በደል የሚሰጠውን ቅጣት የሚያከክስ ነው:: ኢየሱስ የፍቅርን ሕግ መሠረት በማድረግ በብዙዎች ዘንድ ትልቅ ስፍራ ያለው የበቀልን ሕግ ሻረ፤ (ማቴ 5፥38-42 ይመ)::

21፥23 *ጉዳት ቢደርስ፤* በእናት ወይም በልጅ ላይ ማለት ነው::

*21፥26-27፤* የበቀል ሕግን በተመለከተ፣ ሰብዓዊነት ያለው የቅጣት መመሪያ ነው::

*21፥28-32፤* ተዋጊ በሬን በተመለከተ የተሰጠ ሕግ ነው::

21፥28 *በሬ ... በድንጋይ ተወግሮ ይሙት፤* በሬ ሰው ወግቶ ቢገድል ለገደለው ሰው ሕይወት ተጠያቂ ይሆናል፤ (ዘፍ 9፥5 ይመ)::

21፥30 *ካሣ እንዲከፍል ከተጠየቀ፤* ጉዳት የደረሰበት ቤተሰብ በሕይወት ምትክ ካሣ ለመቀበል ፈቃደኛ ከሆነ ማለት ነው:: *ሕይወቱን ይዋጅ፤* ለደረሰው ጉዳት የሚከፈለው ክፍያ (ቃል በቃል ሲተረጐም "ቤዛ" ማለት ነው፤ በዘኍ 35፥31 ላይ እንደተጠቀሰው)፣ ጉዳት የደረሰበትን ቤተሰብ ለመካሥ ሳይሆን የቸልተኛውን ሰው ሕይወት ለማዳን ነው::

21፥32 *ሠላሳ የብር ሰቅል፤* ለአንድ ባሪያ የሚከፈል መደበኛ ክፍያ ነው:: የአስቆሮቱ ይሁዳም፣ ኢየሱስን አሳልፎ በሰጠ ጊዜ ሊቀበል የተስማማው የገንዘብ መጠን ሠላሳ ጥሬ ብር ነበር፤ (ማቴ 26፥14-15፤ ዘካ 11፥12-13 ይመ)::

*21፥33-36፤* በእንስሳት ላይ የሚደርስን ጉዳት በተመለከተ የተሰጠ ሕግ ነው::

*22፥1-15፤* የንብረት ባለ መብትነትን በተመለከተ የተ ሰጠ ሕግ ነው::

*22፥2፤* ሌሊት ራስን ለመከላከል የሚወሰድ እርምጃ ተጠ ያቂ አያስደርግም::

*22፥3፤* ሌባን በጠራራ ፀሓይ መግደል ሕጋዊ አይደለም፤

22፥5 *ምርጥ ከሆነው፤* ካሣ ሲከፈል አከፋፈሉ ቸርነትና ደግነት የተሞላበት መሆን አለበት::

22፥6 *ቍጥቋጦ፤* አብዛኛውን ጊዜ የታረሰ መሬት በከብ ትና በሰው እንዳይረጋገጥ እንደ አጥር ያገለግላል፤ (ሚክ 7፥4)::

*22፥11፤* 20፥7 እና ማብ ይመ:: *በእግዚአብሔር ፊት*

የሌላውን ሰው ንብረት እንዳልወሰደ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት በመማል ነው:: ባለቤቱም ይህን መቀበል አለበት፤ የካሣም ክፍያ አይጠየቅም:: 12እንስሳው ከጎረቤት ተሰርቆ ከሆነ ግን፣ ለባለቤቱ ካሣ መክፈል አለበት:: 13በዱር አራዊት ተበልቶ ከሆነ፣ ከአውሬ የተረፈውን ማስረጃ አድርጎ በማቅረብ፣ ስለ ተበላው እንስሳ ካሣ እንዲከፍል አይጠየቅም::

14"አንድ ሰው ከጎረቤቱ እንስሳ ተውሶ ሳለ ባለቤቱ በሌለበት ቢጎዳ ወይም ቢሞት ካሣ መክፈል አለበት:: 15ባለቤቱ ከእንስሳው ጋር ከሆነ ግን፣ ተበዳሪው መክፈል የለበትም፤ እንስሳው ከተከራየም ለኪራይ የተከፈለው ገንዘብ ኪሳራውን ይሸፍናል::

## ማኅበራዊ ኀላፊነት

16"አንድ ሰው ያልታጨችን ልጃገረድ አታልሎ ክብረ ንጽሕናዋን ቢያጎድል፣ የማጫዋን ዋጋ ከፍሎ ሚስት ያድርጋት:: 17እርሷን ለእርሱ የልጅቷ አባት በሚስትነት ለመስጠት ከቶ የማይፈቅድ ቢሆን፣ ለድንግሎች መከፈል የሚገባውን ማጫ አሁንም ቢሆን መክፈል ይገባዋል::

18"መተተኛ ሴት በሕይወት እንድትኖር አትፍቀድ::

19"ከእንስሳ ጋር ሩካቤ ሥጋ የሚፈጽም ሰው ይገደል::

20"*ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) በቀር ለሌላ አማልክት የሚሠዋ ይጥፋ[ሀ]::

21"መጻተኛውን አትበድሉት፤ ወይም አታስጨንቁት፤ እናንተ በግብፅ መጻተኛ ነበራችሁና::

22"ባል በሞተባት ወይም አባትና እናት በሌለው ልጅ ላይ ግፍ አትዋሉ:: 23ግፍ ብትውሉባቸውና ወደ እኔ ቢጮኹ፣ ጩኸታቸውን በእርግጥ እሰማለሁ:: 24ቍጣዬ ይነሣል፤ በሰይፍም እገድላችኋለሁ፤ ሚስቶቻችሁ መበለቶች፣ ልጆቻችሁም አባት የለሽ ይሆናሉ::

25"ከሕዝቤ መካከል ችግረኛ ለሆነው ለአንዱ ገንዘብ ብታበድሩ፣ እንደ አራጣ አበዳሪ አትሁኑ፤ ወለድ አትጠይቁት[ሐ]:: 26የጎረቤትህን ልብስ መያዣ አድርገህ ብትይዝ ሲመሽ መልስለት፤ 27ምክንያቱም ለሰውነቱ መሸፈኛ ያለው ልብስ ያ ብቻ ነው፤ ሌላ ምን ለብሶ ይተኛል? ወደ እኔ ሲጮህ እኔ እሰማለሁ፤ እኔ ርኅሩኅ ነኝና::

28"በእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ላይ የስድብ ቃል አታሰማ[መ]፤ ወይም የሕዝብህን መሪ አትርገም::

29"የእህልህን ወይም የወይን ጠጅህን በኵራት ለእኔ ከማቅረብ ወደ ኋላ አትበል::

"የወንድ ልጆችህን በኵር ለእኔ ስጠኝ:: 30ከቀንድ ከብትህና ከበጎችህም እንዲሁ አድርግ፤ ለሰባት ቀን ከእናቶቻቸው ጋር ይቆዩ፤ በስምንተኛው ቀን ግን ለእኔ ስጠኝ::

31"እናንተ ለእኔ ቅዱስ ሕዝብ ትሆናላችሁ፤ ስለዚህ አውሬ የዘነጠለውን የእንስሳ ሥጋ አትብሉ፤ ለውሾች ስጡት::

22፥12 ቍ1
22፥13 ዘፍ31፥39
22፥14 ቍ1
22፥15 ዘሌ19፥13፤ ኢዮ17፥5
22፥16 ዘፍ34፥12፤ ዘዳ22፥28
22፥18 ዘፀ7፥11፤ ዘሌ19፥26:31፤ 20፥27፤ዘዳ18፥11፤ 1ሳሙ28፥3፤ 2ዜና33፥6፤ኢሳ57፥3
22፥19 ዘሌ18፥23፤ 20፥15፤ዘዳ27፥21
22፥20 ዘፀ20፥23፤ 34፥15፤ዘሌ17፥7፤ 27፥29፤ዘኍ25፥2፤ዘዳ13፥5፤17፥2-5፤ 18፥20፤32፥17፤ 1ነገ18፥40፤19፥1፤ 2ነገ10፥25፤23፥20፤ 2ዜና15፥13፤ መዝ106፥37፤
22፥21 ዘፀ23፥9፤ ዘሌ19፥33፤24፥22፤ ዘኍ15፥14፤ዘዳ1፥16፤10፥19፤24፥17፤ 27፥19፤ሕዝ22፥29፤ ዘካ7፥10፤ሚል3፥5
22፥22 ቍ26፤ ዘዳ10፥18፤24፥6:10: 12:17፤ኢዮ22፥6:9፤ 24፥3:21፤መዝ68፥5፤ 146፥9፤ምሳ23፥10፤ ኢሳ1፥17፤ኤር7፥5: 6፤21፥12፤22፥3፤ ሕዝ18፥5-9:12፤ ዘካ7፥9-10፤ ሚል3፥5፤ያዕ1፥27
22፥23 ዘዳ10፥18፤ 15፥9፤24፥15፤ ኢዮ34፥28፤35፥9፤ መዝ10፥14:17፤ 12፥5፤18፥6፤34፥15፤ ሉቃ18፥7፤ያዕ5፥4
22፥24 መዝ109፥9፤ ሰቆ5፥3
22፥25 ዘሌ25፥35-37፤ዘዳ15፥7-11፤ 23፥20፤ነህ5፥7:10፤ መዝ15፥5፤ሕዝ18፥8
22፥26 ቍ22፤ምሳ20፥16፤ሕዝ33፥15፤ አሞ2፥8
22፥27 ዘፀ34፥6፤ዘዳ4፥31፤24፥13:17፤2ዜና30፥9፤ ነህ9፥17፤ኢዮ 22፥6፤24፥7፤29፥11፤31፥19-20፤ሕዝ18፥12: 16፤መዝ99፥8፤103፥8፤ 116፥5፤145፥8፤ኢዩ2፥13፤ዮና4፥2
22፥28 ዘፀ20፥7፤2ሳሙ16፥5:9፤19፥21፤1ነገ21፥10፤2ነገ2፥23፤ መዝ102፥8፤መክ10፥20፤ሐሥ23፥5 22፥29 ዘፀ13፥2፤ 23፥15:16:19፤34፥20:26፤ዘሌ19፥24፤23፥10፤ ዘኍ8፥16-17፤ 18፥13፤28፥26፤ዘዳ18፥4፤26፥2:10፤1ሳሙ6፥3፤ነህ10፥35ምሳ3፥9፤ ሚል3፥10፤ሉቃ2፥23 22፥30 ዘፍ17፥12፤ዘፀ34፥19፤ዘሌ12፥3፤ 22፥27፤ዘዳ15፥19 22፥31 ዘፀ19፥6፤ዘሌ19፥2፤22፥31፤ዘሌ7፥24፤ 17፥15፤22፥8፤ዘዳ14፥21፤ዕዝ9፥2፤ሕዝ4፥14፤44፥31

[ሀ]20 የዕብራይስጡ ቃል አንድን ነገር ወይም አንድን ሰው ፈጽሞ በማጥፋት ሙሉ ለሙሉ ለእግዚአብሔር መስጠትን የሚያመለክት ነው::

[ሐ]25 ወይም፣ *ከልክ በላይ የሆነ ወለድ አትጠይቁ* ተብሎ መተርጐም ይችላል::

[መ]28 ወይም፣ *ዳኞችን አትሳደብ* ተብሎ መተርጐም ይችላል::

*በመማል፤* ዳኝነት በሚሰጥበት ቦታ ዳኞች የእግዚአብሔር ተወካዮች ናቸው፤ (21፥6:22፥8-9:28 ይመ)::

*22፥12-13፤* በይዘታቸው ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆኑ ሕጎች ከእስራኤል አባቶች ዘመን በፊት ነበሩ፤ (ዘፍ 31፥39 ይመ)::

*22፥16-31፤* ማኅበራዊ ግዴታዎችን በተመለከተ የተሰጡ አጠቃላይ ሕጎች ናቸው::

22፥16 *የማጫዋን ዋጋ ከፍሎ፤* ታሳቢው ሙሽራ በሙሽራዋ ላይ ላደረሰው ጉዳት፣ ለሙሽራዋ ቤተሰብ የሚከፍለውና የሚሰጠው ስጦታ ነው፤ (ዘፍ 24፥53 ይመ):: ይህ ባሕል አሁንም በአንዳንድ የመካከለኛው ምሥራቅ አገሮች ይጠበቃል::

*22፥18፤* ዘፀ18፥10:14፤1ሳሙ28፥9፤ኢሳ47፥12-14 ይመ::

*22፥19፤* በባቢሎንና በከነዓን በሚነገሩ ጥንታውያን ተረቶችና ታሪኮች ውስጥ በአረማዊ አማልክትና ግማሽ የሰው ግማሽ ደግሞ የእንስሳ አካል ባላቸው የአማልክት ልጆች መካከል የሩካቤ ሥጋ ግንኙነት እንደሚፈጸም ተወስቷል::

*22፥20፤* 20፥3-5 ይመ:: ከጊዜ በኋላ ጣዖት አምላኪ ከነዓናውያን ሙሉ በሙሉ እንዲጠፉ/እንዲደመሰሱ እግዚአብሔር ትእዛዝ ሰጥቶአል፤ (ዘኍ21፥2፤ ዘዳ2፥34:3፥6:7፥2:13፥5:20፥17: ኢሱ2፥10፤ 6፥17:21፤ 8፥25:10:1:28:35:37:39-49:11፥11-12:20-21፤መሳ 1፥17 ይመ)::

*22፥21-27፤* ሙሴ በጻፉቸው መጻሕፍት ውስጥ፣ ረዳት የሌላቸው ሕዝቦች ማለትም ድሆች፣ መበለቶች፣ ወላጅ የለሾችና መጻተኞች እግዚአብሔር ልዩ ጥንቃቄና እንክብካቤ እንደሚያደርግላቸው ተገልጾአል፤ (21፥26-27:23፥6-12: ዘሌ 19:9-10፤ ዘዳ 14፥29: 16፥11:14:24፥19-21፤ 26፥12-13 ይመ)፤ ከዚህ በተጨማሪ በዳዊት መዝሙራት (መዝ 10፥14: 17-18: 68፥5: 82፥3: 146፥9 ይመ)፤ በነቢያት መጻሕፍትና (ኢሳ 1፥23:10፥2: ኤር 7፥6:22፥3: ዘካ 7፥10፤ ሚል 3፥5 ይመ)፣ በኢየሱስ ትምህርት (ለምሳሌ ማቴ 25፥34-45) ውስጥ እግዚአብሔር ለድኾች እንደሚያስብላቸው ተብራርቶ ተጠቅሶአል::

*22፥25-27፤* ከብድር የሚገኝ ወለድ/ትርፍ በተመለከተ የተሰጠ ሕግ ነው፤ (ዘሌ 25፥35-37፤ ዘፀ 15፥7-11:23፥19-20: ነህ 5፥7-12፤ ኢዮ 24፥9፤ ምሳ 28፥8፤ ሕዝ 18፥13: 22፥12 ይመ) ድሆች ከሚበደሩት ገንዘብ ወለድና ትርፍ ማግኘት ተከልክሎአል፤ ይልቁንም በእንዲህ ዐይነቱ አጋጣሚ ቸርነት ማድረግ እንደሚገባ ኢየሱስ ክርስቶስ አስተምሮአል፤ (ሉቃ 6:34-35 ይመ)::

*22፥26-27፤* አንድ ሰው ለሚበደረው ገንዘብ መያዣ አድርጐ የሚሰጠው የሌሊት ልብሱን ከሆነ፣ ከድኾች መካከል እጅግ ድኻ እርሱ ነው፤ (አሞ 2፥8 እና ማብ ይመ)::

22፥28 *የሕዝብህንም መሪ አትርገም፤* የሕዝብ አለቃ ወይም ገዥ በምድር የእግዚአብሔር ተወካይ ነው፤ ሳያስበው ሊቀ ካህናቱን የተሳደበው ሐዋርያው ጳውሎስ በመጸጸት ይህን ቃል ጠቅሶአል፤ (ሐሥ 23፥4-5 ይመ)::

22፥29 *የወንድ ልጅህን በኵር ለእኔ ስጠኝ፤* የ4፥22: 13፥2:13 ማብ እና 13፥15 ይመ::

22፥30 *ከቀንድ ከብትህና ከበጎችህም እንዲሁ አድርግ፤* የ13፥2:13፥13 ማብ እና 13፥12:15 ይመ:: *በስምንተኛው ቀን ለእኔ ስጠኝ፤* ይኸው መመሪያ በኵር ሆነው ለተወለዱ ወንዶች ልጆች እንዲያገለግል ለየት ባለ መንገድ ቀርቦአል፤ (የዘፍ17፥12 ማብ ይመ)::

*22፥31፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ "የካህናት መንግሥት"

## የፍትህና የምሕረት ሕጎች

**23** የሐሰት ወሬ አትንዛ፤ ተንኰል ያለበትን ምስክርነት በመስጠት ክፉውን ሰው አታግዝ።

2“ክፉ በማድረግ ብዙዎችን አትከተል፤ በሕግ ፊት ምስክርነት ስትሰጥ፣ ከብዙዎቹ ጋር ተባብረህ ፍትሕ አታጣምም። 3በዳኝነት ጊዜ ለድኻው አታድላ።

4“የጠላትህ በሬ ወይም አህያ ሲባዝን ብታገኘው ወደ እርሱ መልሰው። 5የሚጠላህ ሰው አህያ፣ ጭነት ከብዶት ወድቆ ብታየው እርዳው እንጂ ትተኸው አትሂድ።

6“በዳኝነት ጊዜ በድኻው ላይ ፍርድ አታጓድልበት። 7ከሐሰት ክስ ራቅ፤ በደል የሌለበትን ወይም ትክክለኛውን ሰው ለሞት አሳልፈህ አትስጥ፣ በደለኛውን ንጹሕ አላደርግምና።

8“ጉቦ አትቀበል፤ ጉቦ፣ አጥርተው የሚያዩትን ሰዎች ዐይን ያሳውራል፤ የጻድቃንንም ቃል ያጣምማልና።

9“መጻተኛውን አትጨቍን፤ በግብፅ መጻተኛ ስለ ነበራችሁ፣ መጻተኛ ምን እንደሚሰማው እናንተ ራሳችሁ ታውቃላችሁና።

## የሰንበት ሕጎች

10“ስድስት ዓመት በእርሻህ ላይ ዝራ፤ አዝመራንም ሰብስብ፤ 11ነገር ግን በሰባተኛው ዓመት ምድሪቱን ሳትጠቀምባትና ሳታርሳት እንዲሁ ተዋት፤ ከዚያም በወገንህ መካከል ያሉት ድኾች ከእርሷ ምግብ ያገኛሉ፤ የዱር አራዊትም ከእነርሱ የተረፈውን ይበላሉ። በወይን ቦታህና በወይራ ዛፎችህም ላይ እንዲሁ አድርግ።

12“ስድስት ቀን ሥራህን ሥራ፤ በሬህና አህያህ በቤትህ የተወለደው ባሪያና መጻተኛው ያርፉ ዘንድ በሰባተኛው ቀን ምንም አትሥራ።

13ያልኋችሁን ሁሉ ታደርጉ ዘንድ ተጠንቀቁ፤ የሌሎችን አማልክት ስም አትጥሩ፤ ከአፋችሁም አይሰሙ።

## ሦስቱ ዐውደ ዓመታዊ በዓላት

14በዓመት ሦስት ጊዜ ለእኔ በዓልን ታከብራላችሁ።

15“ያልቦካ የቂጣ በዓልን አክብር፤ እንዳዘዝኩህ ሰባት ቀን እርሾ የሌለውን ቂጣ ብላ፤ ይህንንም በአቢብ ወር በተወሰነ ቀን አድርግ፤ በዚያ ወር ከግብፅ ወጥተሃልና።

“ማንም በፊቴ ባዶ እጁን አይቅረብ።

16“በማሳህ ላይ በዘራኸው እህል በኵራት የመከርን በዓል አክብር።

“በዓመቱ መጨረሻ በማሳህ ላይ ያለውን እህልህን ስትሰበስብ የመክተቻውን በዓል አክብር።

17“በዓመት ሦስት ጊዜ ወንድ ሁሉ በጌታ *በእግዚአብሔር* (አዶናይ ያህዌ) ፊት ይቅረብ።

18የመሥዋዕትን ደም እርሾ ካለበት ነገር ጋር አድርገህ ለእኔ አታቅርብ።

“የበዓል መሥዋዕቴ ስብ እስከ ንጋት ድረስ አይቆይ።

19“የምድርን ምርጥ ፍሬ በኵራት በስም ባክህ *ለእግዚአብሔር* (ኤሎሂም ያህዌ) አምጣ።

“ጠቦት ፍየልን በእናቱ ወተት አትቀቅል።

## የእግዚአብሔር (ኤሎሂም) መልአክ መንገድ ስለ መምራቱ

20“እነሆ፤ በጕዞ ላይ ሳለህ የሚጠብቅህንና

23፥1 ዘፍ39፥17፤ ዘፀ20፥16፤ዘዳ5፥20፤ 19፥16-21፤ መዝ 27፥12፤35፥11፤ምሳ 19፥5፤ማቴ19፥18፤ ሉቃ3፥14፤ሐሥ6፥11
23፥2 ቍ3:6:9፤ ዘሌ19፥15:33፤ዘዳ 1፥17፤16፥19፤24፥17 ፤27፥19፤1ሳሙ8፥31 ኢዮ31፥34
23፥3 ዘዳ1፥17
23፥4 ዘሌ6፥3፤ 19፥11፤ዘዳ22፥1-3፤ ሮሜ12፥20
23፥5 ዘዳ22፥4
23፥6 ቍ2፤ ዘዳ 23፥16፤ምሳ22፥22
23፥7 ዘፍ18፥23፤ ዘፀ20፥16፤34፥7፤ ዘዳ19፥18፤25፥1፤ ማቴ27፥4፤ኢፌ4፥25
23፥8 ዘፀ18፥21፤ ዘሌ19፥15፤ዘዳ10፥17 ፤27፥25፤ኢዮ15፥34 ፤36፥18፤መዝ26፥10፤ ምሳ6፥35፤15፥27፤ 17፥8፤ኢሳ1፥23፤ 5፥23፤ሚክ3፥11፤7፥3
23፥9 ቍ2፤ዘፀ 22፥21፤ዘሌ19፥33- 34፤ሕዝ22፥7
23፥11 ዘሌ25፥1- 7፤ነህ10፥31
23፥12 ዘፍ2፥2-3፤ ዘፀ20፥9፤ሉቃ13፥14
23፥13 ቍ32፤ ዘዳ4፥9:23፤12፥3፤18 ፥20፤ኢሱ23፥7፤መዝ 16፥4፤ዘካ13፥2፤ሆሴ 2፥17፤1ጢሞ4፥16
23፥14 ቍ17፤ ዘፀ12፥14፤34፥23: 24፤ዘዳ16፥16፤1ነገ 9፥25፤2ዜና8፥13፤ ሕዝ46፥9
23፥15 ዘፀ12፥2: 17፤22፥29፤ ማቴ26፥17፤ ሉቃ22፥1፤ሐሥ12፥3
23፥16 ዘሌ23፥15-21፤ዘፀ22፥29፤34፥22፤ዘሌ23፥34:39:42፤ ዘኍ28፥26፤ዘዳ16፥9:13:16፤31፥10፤2ዜና8፥13፤ዕዝ3፥4፤ነህ8፥14፤ ኤር40፥10፤ዘካ14፥16 23፥17 ቍ14 23፥18 ዘፀ12፥8፤34፥25፤ ዘሌ2፥11 23፥19 ዘፀ22፥29፤34፥22:26፤ዘኍ18፥12፤ዘዳ14፥21 23፥20 ዘፍ16፥7፤ ዘፀ15፥17

---

በመሆናቸው፣ (19፥6 እና ማብ ይመ)፤ ለአሮን ዝርያዎች የተሰተጠውን መመሪያ እነርሱም መታዘዝ አለባቸው፤ (ዘሌ 22፥8)።

*23፥1-9፤* በዚህ ክፍል የተገለጹት አብዛኞዎቹ ሕጎች ከ20፥16 ጋር የተያያዙ ናቸው።

*23፥1፤* ዘሌ 19፥16፤ ዘፀ 22፥13-19፤ 1ነገ21:10-13 ይመ።

*23፥4-5፤* ለሌሎች የሚያሳዩትን ቸርነት ጠላቶቻቸው ለሆኑትም ማሳየት ይገባቸዋል፤ (ዘፀ 22:1-4፤ ምሳ 25፥21 ይመ)፤ እንዲህ ሲባል “ጠላትህን ውደድ” ማለት እንደሆነ ኢየሱስ አስተምሮአል፤ (ማቴ 5፥44)።

*23፥7፤* በ1ነገ 21፥10-13 የተጠቀሰው ታሪክ፣ ይህን ሕግ በግልጽ የሚጻረር ነው።

*23፥8፤* ዘዳ 16፥19 ይመ። ነቢዩ ሳሙኤል ይህን ሕግ በተመለከተ ታማኝ መጋቢ ሆኖ ሲገኝ፣ (1ሳሙ 12፥3) ልጆቹ ግን ታማኞች አልነበሩም፤ (1ሳሙ 8፥3 ይመ)።

*23፥10-13፤* በ20፥8-11፤ ዘዳ 5፥12-15 የተሰጠውን ትምህርት በስፋት የሚያብራራ ነው።

*23፥14-19፤* 34፥18-23፤ ዘሌ 23፥4-44፤ ዘኍ 28፥16-19:40፤ ዘዳ 16፥1-17 ይመ።

23፥15 ***የቂጣ በዓልን፤*** የገብስ መከር በሚሰበሰብበት በመጀመሪያው ወር ከዐሥራ አምስተኛው ቀን ጀምሮ እስከ ሃያ አንደኛው ቀን ድረስ (ከመጋቢት አጋማሽ እስከ ሚያዝያ አጋማሽ ድረስ ማለት ነው፤ የ12፥2 ማብ ይመ) ይከበራል፤ ይህም እስራኤላውያን ከግብፅ የወጡበትን ጊዜ ያሳስባል።

23፥16 ***የመከር በዓል፤*** ከቂጣ በዓል በኋላ ሰባት ሰምንት ሙሉ ስለሚከበር፣ “የሱባዔ በዓል” (34፥22) ተብሎ ይጠራል። በዓሉ በስንዴ መከር ወቅት በሦስተኛው ወር በስድስተኛው ቀን (ከሚያዝያ አጋማሽ እስከ ሰኔ አጋማሽ ማለት ነው) ይከበራል። የኋላ ኋላ ግን አይሁዳውያን በሲና ተራራ ሕግ ከተሰጠበት ሁኔታ ጋር አያይዘውታል፤ ይሁን እንጂ፣ በብሉይ ኪዳን በዚህ መልክ ተያይዞ የተነገረ ነገር የለም። በአዲስ ኪዳን ዘመን ይህ በዓል “በዓለ ኀምሳ” በመባል ይታወቃል፤ (ሐሥ 2፥1:20፥16፤ 1ቆሮ 16፥8፤ ትርጕሙም “ኀምሳ” ማለት ነው፤ (ዘሌ 23፥16 ይመ)። ***የመክተቻውን በዓል፤*** በተጨማሪም “የዳስ በዓል” (ዘሌ 23፥34) ተብሎ ይታወቃል፤ ምክንያቱም እስራኤላውያን እግዚአብሔር ከግብፅ ካወጣቸው በኋላ በጊዜያዊ መጠለያ ይኖሩ ነበርና ነው፤ (ዘሌ 23፥43)። በዓሉ የሚከበረው የወይንና የእርሻ ፍሬ ከተሰበሰበ በኋላ በሰባተኛው ወር ከዐስራ አምስተኛው ቀን እስከ ሃያ ሁለተኛው ቀን ድረስ ነው። ይህም እስራኤላውያን ከግብፅ ከወጡ በኋላ ያሳለፉትን የምድረ በዳ ኑሮ ያስታውሳል። ***በዓመቱ መጨረሻ፤*** በእርሻ ዓመት ማብቂያ ማለት ነው፤ የሚጀምረውም በበልግ/በመፀው አካባቢ ነው፤ (የ12፥2 ማብ ይመ)።

23፥17 ***ወንድ ሁሉ፤*** ከቤተሰቦቻቸው ጋር አብረው ሆነው ማለት ነው፤ (ለምሳሌ 1ሳሙ 1 ይመ)።

23፥18 ***እርሾ ካለበት ነገር ጋር አድርገህ ለእኔ አታቅርብ፤*** የ12፥15ን ማብ ይመ። ***እስከ ንጋት ድረስ አይቆይ፤*** 12፥9-10 ይመ።

23፥19 ***የምድርን ምርጥ ፍሬ በኵራት፤*** የመከር ሁሉ ወካይ ሲሆን፣ በኵራት ለእግዚአብሔር የሚሰጠው መከርን የሚሰጥ እርሱ በመሆኑና ሁሉም የእርሱ በመሆኑ ነው። ***ጠቦት ፍየልን በእናቱ ወተት አትቀቅል፤*** የከነዓናውያንን ሥርዐተ አምልኮ ለመቃወም የተሰጠ ትእዛዝ ሳይሆን አይቀርም፤ (ቍ33፤34፥15 ይመ)።

ወዳዘጋጀሁልህ ስፍራ የሚያስገባህን መልአክ በፊትህ ልኬልሃለሁ:: 21በጥንቃቄ ተከተለው፤ የሚናገረውንም ልብ ብለህ አድምጠው፤ አታምፅበት:: ስሜ በርሱ ላይ ነውና ዐመፅህን ይቅር አይልም:: 22የሚናገረውን በጥንቃቄ ብታደምጥና ያልኩህን ሁሉ ብታደርግ ለጠላቶችህ ጠላት እሆናለሁ፤ የሚቃወሙህን እቃወማለሁ:: 23መልአኬ በፊትህ ይሄዳል፤ አንተንም ወደ አሞራውያን፣ ወደ ኬጢያውያን፣ ወደ ፌርዛውያን፣ ወደ ከነዓናውያን፣ ወደ ኤዊያውያንና ኢያቡሳውያን ምድር ያስገባሃል፤ እኔም እነርሱን አጠፋቸዋለሁ:: 24ለአማልክቶቻቸው አትስገድ፤ ወይም አታምልካቸው፤ ወይም ልምዳቸውን አትከተል፤ እነርሱን ማፈራረስ አለብህ፤ የአምልኮ ድንጋዮቻቸውንም ሰባብር:: 25አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ) አምልክ፤ በረከቱም በምትበላውና በምትጠጣው ላይ ይሆናል፤ በሽታንም ከአንተ ዘንድ አርቃለሁ:: 26በምድርህም ፅንስ የሚያስወርዳት ወይም መካን ሴት አትኖርም፤ ረጅም ዕድሜም እሰጥሃለሁ::

27"በሚያጋጥሙህ አሕዛብ ሁሉ ላይ ማስፈራቴን በፊትህ እልካለሁ፤ ግራም አጋባቸዋለሁ፤ ጠላቶችህ ሁሉ ወደ ኋላ ተመልሰው እንዲሸሹ አደርጋለሁ:: 28ኤዊያውያንን፣ ከነዓናውያንን፣ ኬጢያውያንን ከመንገድህ ለማስወጣት ተርብን በፊትህ እሰዳለሁ:: 29ነገር ግን በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ አላወጣቸውም፤ ምክንያቱም ምድሪቱ፣ ባድማ ሆና፣ የዱር አራዊት ይበዙብችኋል:: 30ቀጥርህ ጨምሮ ምድሪቱን ለመውረስ እስክትበቃ ድረስ ጥቂት በጥቂት ከፊታችሁ አባርራቸዋለሁ::

31"ድንበርህን ከቀይ ባሕር[o] እስከ ፍልስጥኤም ባሕር፣[n] ከምድረ በዳው እስከ ወንዙ[x] ድረስ አደርገዋለሁ፤ በምድሪቱም ላይ የሚኖሩትን ሰዎች አሳልፌ እሰጥሃለሁ፤ አንተም አሳድህ ከፊትህ ታስወጣቸዋለህ:: 32ከእነርሱም ሆነ ከአማልክቶቻቸው ጋር ኪዳን አታድርግ:: 33በምድርህ ላይ እንዲኖሩ አትፍቀድላቸው፤ አለዚያ እኔን እንድትበድል ያደርጉሃል፤ አማልክቶቻቸውን ማምለክ በርግጥ ወጥመድ ይሆንብሃልና::"

### ቃል ኪዳኑ ስለ መጽናቱ

24 ከዚያም ሙሴን "አንተና አሮን፣ ናዳብና አብዩድ ከሰባዎቹ የእስራኤል አለቆች ጋር ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ኑ፤ ከሩቅም ስገዱ አለው፤ 2ነገር ግን ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሊቀርብ የሚችለው ሙሴ ብቻ ነው:: ሌሎቹ መቅረብ የለባቸውም ሕዝቡም ከእርሱ ጋር መምጣት የለበትም::"

3ሙሴ ወደ ሕዝቡ ሄዶ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ቃሎችና ሕጎች ሁሉ በነገራቸው ጊዜ በአንድ ድምፅ ሆነው፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ያለውን ሁሉ እናደርጋለን" አሉ:: 4ከዚያም ሙሴ እግዚአብሔር (ያህዌ) ያለውን ሁሉ ጻፈ:: በማግሥቱም ማልዶ ተነሥቶ፣ በተራራው ግርጌ መሠዊያን ሠራ፤ አሥራ ሁለቱን የእስራኤልን ነገዶች የሚወክሉ ዐሥራ ሁለት የድንጋይ ዐምዶችን አቆመ:: 5ከዚያም ወጣት ወንድ እስራኤላውያንን ላከ፤ እነርሱም የሚቃጠል መሥዋዕት[f] አቀረቡ፤ ወይፈኖችን የኅብረት መሥዋዕት አድርገው ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ሠዉ:: 6ሙሴ የደሙን እኩሌታ ወስዶ በጎድጓዳ ሣህኖች አኖረው፤ የቀረውንም እኩሌታ በመሠዊያው ላይ

23፥21 ዘፀ3፥15፤ ዘኍ17፥10፤ ዘዳ 9፥7፤18፥19፤ 29፥20፤31፥27፤ ኢሱ24፥19፤ 2ነገ24፥4፤መዝ25፥7፤ 78፥8፡40፡56፤ 106፥33፤107፥11፤ ኤር13፥15፤ሰቆ1፥17 1ዮሐ5፥16
23፥22 ዘፍ12፥3፤ ዘፀ15፥26፤ኢሳ41፥11 ኤር30፥20
23፥23 ዘኍ13፥29 ፤21፥21፤ኢሱ3፥10፤ 24፥8፡11፤ዕዝ9፥1፤ መዝ135፥11
23፥24 ዘፀ20፥5፤ 34፥13፤ ዘሌ18፥3፤ 20፥23፤26፥1፤ ዘኍ 33፥52፤ዘዳ7፥5፤9፥4፤ 12፥3፡30-31፤16፥22 ፤መሳ2፥2፤2ነገ18፥4፤ 23፥14፤1ነገ14፥23፤ 2ነገ3፥2፤10፥26፤ 17፥10፤2ዜና14፥3፤ ኢሳ27፥9፤ኤር10፥2
23፥25 ዘፀ15፥26፤ ዘሌ26፥3-13፤ዘዳ 7፥12-15፤28፥1-14፤ ማቴ4፥10
23፥26 ዘፍ15፥15፤ ዘሌ26፥3-4፤ዘዳ4፥1፡ 40፤7፥14፤28፥4፤ 32፥47፤ሚል3፥11፤ መዝ90፥10
23፥27 ዘፍ35፥5፤ ዘፀ15፥14፤14፥24፤ ዘዳ7፥23፤2ሳሙ 22፥41፤መዝ18፥40፤ 21፥12
23፥28 ዘፀ33፥2፤ 34፥11፡24፤ዘኍ 13፥29፤ዘዳ4፥38፤7፥ 20፤11፥23፤18፥12፤ ኢሱ3፥10፤24፥11፡12 ፤መዝ78፥55
23፥29 ዘዳ7፥22
23፥30 ኢሱ23፥5
23፥31 ዘፍ2፥14፤ ዘዳ7፥24፤9፥3፤34፥2፤ ኢሱ21፥44፤ 24፥12፡18፤ዕ4፥20፤ መዝ80፥8
23፥32 ዘፍ26፥28፤ዘፀ34፥12፤ዘዳ7፥2፤ኢሱ9፥7፤መሳ2፥2፤ 1ሳሙ11፥1፤1ነገ15፥19፤ 20፥34፤ሕዝ17፥13 23፥33 ዘፀ10፥7
24፥1 ቍ9፤ዘፀ6፥23፤ 19፥24፤ዘኍ11፥6 24፥2 ዘኍ12፥6-8
24፥3 ዘፀ19፥8፤21፥1፤ ኢሱ24፥24፤ገላ3፥19 24፥4 ዘፍ8፥20፤ 28፥18፤ዘፀ17፥14፤ዘዳ27፥2 24፥5 ዘፍ31፥54፤ዘሌ1፥3
24፥6 ዘፀ14፥15፤ 32፥31፤ዘሌ1፥11፤ 3፥2፡8፡13፤5፥9፤ መዝ99፥6፤ ማቴ26፥28፤ዕብ9፥18

[o]31 በዕብራይስጥ፣ *ያም ሱፍ* ይባላል፤ ይኸውም፣ *የደንገል ባሕር* ማለት ነው::
[n]31 የሜዲትራንያን ባሕር ማለት ነው::
[x]31 የኤፍራጥስ ወንዝ ማለት ነው::
[f]5 በትውፊት፣ *የሰላም መሥዋዕት* በመባል ይታወቃል::

23፥20 ***መልአክ፤*** 14፥19 ይመ፤ የዘፍ 16፥7 ማብ ይመ:: ***ወዳዘጋጀሁልህ ስፍራ፤*** ከነዓንን ማለት ነው፤ (ከዮሐ 14፥2-3 ጋር ያነጻጽሩ)::

23፥21 ***ስሜ፤*** የእግዚአብሔርን መገኘት ያመለክታል::

23፥22 ***ብታደምጥና፤*** የ19፥5 ማብ ይመ::

***23፥23፤*** 3፥8 እና ማብ ይመ::

23፥28 ***ተርብ፤*** ለዚህ ቃል የገባው የዕብራይስጡ ቃል ትርጕም ምን እንደሆነ በትክክል አይታወቅም:: ሆኖም እግዚአብሔር እስራኤልን የተስፋዪቱን ምድር እንዳይወርሱ በሚያደርጓቸው ላይ እንዲህ ያሉ አስጨናቂ ነገሮችን እንደሚልክባቸው ተናግሮአል::

23፥30 ***ጥቂት በጥቂት፤*** መሳ 1 ይመ::

***23፥31፤*** ዘፍ 15፥18፤ 1ነገ 4፥21 ይመ:: ***ቀይ ባሕር፤*** የደቡብ ምስራቅ ድንበር ነው፤ (በአሁኑ ጊዜ የአቃባን ባሕረ ሰላጤ ማለት ነው፤ የ1ነገ 9፥26 ማብ ይመ) ***ሜዲትራንያን፤*** የፍልስጥኤም ባሕር ምእራባዊ ድንበር ነው:: ***ምድረ በዳው፤*** ሰሜን ምስራቅ ሲና ወይም ደቡባዊ ድንበር ነው፤ (የዘፍ 15፥18 ማብ ይመ) ***ወንዝ፤*** ሰሜናዊ ድንበር ነው::

23፥33 ***ወጥመድ፤*** የጥፋት ምልክት ነው (10፥7፤ ኢዮ 18፥9፤ መዝ 18፥5፤ ምሳ 13፥14፡21፥6 ኢሳ 24፥17-18 ይመ)::

24፥1 ***ወደ እግዚአብሔር ኑ፤*** በ 20፥21 ላይ በኪዳኑ መጽሐፍ ምክንያት የተቋረጠው ታሪክ (20፥22-23፥33) ከዚያ ላይ እንደገና ይጀምራል:: በቍ 3-8 ያለው ኹነት ከተፈጸመ በኋላ ሙሴና ረዳቶቹ ወደ ተራራው ወጡ:: ***ናዳብና አብዩድ፤*** የአሮን የመጀመሪያ ሁለት ወንዶች ልጆቹ ናቸው፤ ናዳብ በአሮን ምትክ የሊቀ ካህናት ቦታ ተተክቶ ሲያገለግል እርሱና ወንድሙ እግዚአብሔር ያልፈቀደውን እሳት በጥናው ላይ በመጨመራቸው ሞቱ፤ (ዘሌ 10፥1-2፤ ዘኍ 3፥4 ይመ):: ***ከሰባዎቹ የእስራኤል አለቆች፤*** ምናልባትም የያዕቆብን ሰባ ልጆች ለማመልከት ሳይሆን አይቀርም፤ (ከዘኍ 11፥16 ጋር ያነጻጽሩ፤ ዘፍ 46፥27 እና ማብ፤ 3፥16 ይመ):: ***ከሩቅ፤*** 20፥21 ይመ::

24፥2 ***ሙሴ ብቻ፤*** ሙሴ በእግዚአብሔርና በእስራኤል ሕዝብ መካከል የሚቆም ማዕከል ነው:: ሁለተኛው ሙሴ ኢየሱስ ክርስቶስ (ዕብ 3፥1-6 ይመ) "የአዲስ (ሥርዐት) ማዕከል ኪዳን" ነው፤ (12፥24 ይመ)::

24፥3 ***ቃሉች፤*** ዐሥር ትእዛዛትን ሊያመለክት ይችላል፤ (20፥1 እና ማብ ይመ):: ***ሕጎች፤*** ምናልባት በኪዳኑ መጽሐፍ ላይ የተዘረዘሩትን ሕግጋት ሊያመለክት ይችላል (21፥1-23፡1 ይመ) ***እናደርጋለን፤*** ቍ 7፤ 19፥8 እና ማብ ይመ::

24፥4 ***ሙሴ ... ጻፈ፤*** የ17፥14ን ማብ ይመ:: ***ዐሥራ ሁለት ድንጋዮች፤*** ኢሱ 4፥5፡20፤ 1ነገ 18፥31 ይመ::

24፥5 ***ወጣት ወንድ እስራኤላውያን ... አቀረቡ፤*** የ19፥22ን ማብ ይመ::

24፥6 ***የደሙን እኩሌታ ... የቀረውን እኩሌታ፤*** ደሙ ከሁለት ቦታ የተከፈለበት ምክንያት "የኪዳኑ ደም" (ቍ 8) ሁለት

ረጨው። [7]ከዚያም የኪዳኑን መጽሐፍ ወስዶ ለሕዝቡ አነበበላቸው፤ እነርሱም፣ "እግዚአ ብሔር (ያህዌ) ያለውን ሁሉ እናደርጋለን፤ እን ታዘዛለን" አሉ።

[8]ከዚያም ሙሴ ደሙን ወሰደ፤ ሕዝቡም ላይ ረጭቶ፣ "ይህ እነዚህን ቃሎች በሰጠ ጊዜ፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) ከእናንተ ጋር የገ ባው የቃል ኪዳኑ ደም ነው" አላቸው።

[9]ሙሴና አሮን፣ ናዳብና አብዩድ እንደ ዚሁም ሰባዎቹ የእስራኤል አለቆች ወደ ተራ ራው ወጡ፣ [10]የእስራኤልንም አምላክ (ኤሎሂም) አዩ፤ ከእግሩም በታች እንደ ብሩህ ሰማይ የጠራ የሰንፔር* ወለል ነበር። [11]ሆኖም እግዚአብሔር በእስራኤል ሕዝብ አለቆች ላይ እጁን አላነሣባቸውም። እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) አዩ፣ በሉ፤ ጠጡም።

[12]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "በተራራው ላይ ወደ እኔ ና፤ በዚህም ቆይ፤ እኔም መመሪያ እንዲሆናቸው ሕግና ትእዛዛት የጻፍኩባቸውን የድንጋይ ጽላቶች እሰጥሃ ለሁ" አለው።

[13]ከዚያም ሙሴ ከረዳቱ ከኢያሱ ጋር አብሮ ሄደ፤ ሙሴም ወደ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ተራራ ወጣ። [14]እርሱም ሽማግሌዎችን "ወደ እናንተ እስክንመለስ ድረስ በዚህ ቆዩ፤ አሮንና ሖር ከእናንተ ጋር ናቸው፤ ክርክር ያለው ሰው ቢኖር ወደ እነርሱ ይሂድ።" አላቸው።

[15]ሙሴ ወደ ተራራ ሲወጣ ደመናው ተራራውን ሸፈነ፤ [16]የእግዚአብሔርም (ያህዌ) ክብር በሲና ተራራ ላይ ወረደ፣ ደመና ውም ተራራውን እስከ ስድስት ቀን ድረስ ሸፈነው፤ በሰባተኛውም ቀን እግዚአብሔር (ያህዌ) በደመናው ውስጥ ሆኖ ሙሴን ጠራው። [17]ለእስራኤላውያን የእግዚአብሔር (ያህዌ) ክብር በተራራው ጫፍ ላይ እንደሚባላ እሳት ሆኖ ይታይ ነበር። [18]ከዚያም ሙሴ ወደ ተራራው ሲወጣ ደመናው ውስጥ ገባ፤ በተ ራራውም ላይ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ቈየ።

## ለመገናኛው ድንኳን የሚቀርቡ ስጦታዎች

25፥1-7 ተጓ ምብ - ዘፀ 35፥4-9

**25** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ [2]"ስጦታ እንዲያመጡልኝ ለእስራኤ ላውያን ንገራቸው። ይሰጥ ዘንድ ልቡ ካነ ሣሣው ከእያንዳንዱ ሰው ስጦታን ተቀበ ሉልኝ። [3]ከእነርሱ የምትቀበላቸው ስጦታ ዎች እነዚህ ናቸው፦ ወርቅ፣ ብርና፣ ነሐስ፣ [4]ሰማያዊ፣ ሐምራዊ፣ ቀይ ማግና የበፍታ ክር ልብስ፣ የፍየል ጠጕር፣ [5]ቀይ የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ፣ የለፋ ቆዳ፣ የግራር እንጨት፣ [6]የመብራት ወይራ ዘይት፣ ለቅ ብዓ ዘይቱና ጣፋጭ መዓዛ ላለው ዕጣን የሚ ሆኑ ቅመሞች፣ [7]በኤፉድና በደረት ኪስ ላይ

24፥7 ዘፀ19፥8፤ 2ነገ23፥2:21፤ ኤር40፥3፤42፥6:21፤ 43፥2፤ዕብ9፥19
24፥8 ዘሌ26፥3፤ ዘዳ5፥2-3፤ኢሱ24፥25፤2ነገ11፥17፤ ኤር11፥4:8፤31፥32፤ 34፥13፤ዘካ9፥11፤ ማቴ26፥28፤ሉቃ22፥20፤ ዕብ9፥19:20፤ 1ጴጥ1፥2
24፥9 ቍ1
24፥10 ዘፍ16፥13፤ዘኍ12፥6፤ኢዮ26፥16፤ኢሳ6፥1፤ 54፥11፤ሕዝ1፥1:26፤8፥3፤10፥1፤40፥2፤ዮሐ1፥18፤ራእ4፥3
24፥11 ቍ10፤ዘፀ3፥6፤19፥21፤ሕዝ44፥3፤ማቴ26፥29
24፥12 ዘፀ31፥18፤ 32፥15-16፤ 34፥1:28:29፤ ዘዳ4፥13፤ 5፥22፤8፥3፤9፥9:10:11፤10፥4፤ 2ቆሮ3፥3
24፥13 ዘፀ3፥1፤ 17፥9
24፥14 ዘፀ17፥10፤ 18፥16
24፥15 ዘፀ19፥9፤ ማቴ17፥5
24፥16 ዘፀ16፥7፤ 19፥11፤ዘሌ9፥23፤ ዘኍ14፥10፤ 1ሳሙ4፥21:22፤ መዝ99፥7፤ ሕዝ8፥4፤11፥22
24፥17 ዘፀ15፥7፤ 19፥18፤ ዕብ12፥18:29 24፥18 ዘፍ7፥4፤ 1ነገ19፥8፤ማቴ4፥2
25፥2 ዘፀ35፥21:22:26:27:29፤36፥2፤2ነገ12፥4፤1ዜና29፥5:7:9፤ 2ዜና24፥10፤29፥31፤ዕዝ2፥68፤ነህ7፥70-72፤2ቆሮ8፥11-12፤9፥7
25፥4 ዘፀ28፥4-8 25፥5 ዘኍ4፥6: 10፤ዘዳ10፥3
25፥6 ዘፀ27፥20፤ 30፥1:7:22-32:35፤35፥28፤ 39፥37፤ 31፥11፤35፥28፤ዘሌ16፥12፤ዘኍ4፥16፤ 7፥14፤2ዜና13፥11

*10 ወይም፣ ላፒስ ላዚሊ ተብሎ መተርጐም ይችላል።

ገጽታ እንዳለው ለማመልከት ነው፤ በመሠዊያው ላይ ያለው ደም የእግዚአብሔርን ይቅር ባይነትና የመሥዋዕቱን ተቀባይነት ሲያ መለክት፣ በሕዝቡ ላይ የተረጨው ደም ደግሞ ሕዝቡ እግዚአ ብሔርን ለመታዘዝ የገባውን መሐላ ያመለክታል (ቍ3:7 ይመ)።

24፥7 *የኪዳኑን መጽሐፍ፤* ከ20፥22-23፥19 ያለውን ክፍል የሚያመለክት ቢሆንም፣ እዚህ ላይ ግን በ20፥2-17 እና 23፥20-33 ላይ የተዘረዘሩትንም ትእዛዛት ያመለክታል። *እናደርጋለን … እንታዘዛለን፤* ቍ 3:19፥8 እና ማብ ይመ።

24፥8 *ከዚያም፤* ሕዝቡ ከእግዚአብሔር ጋር ቃል ኪዳን መግባት የሚችለው፣ እግዚአብሔርን ለመታዘዝ የተስማሙ እንደ ሆን ብቻ ነው። *የቃል ኪዳኑ ደም፤* ማር14፥24 እና ማብ ይመ።

24፥9 *ወደ ተራራው ወጡ፤* ቍ 1 እና ማብ ይመ።

24፥10 *የእስራኤልን አምላክ አዩ፤* ያዩት በሙሉ ክብሩ አይደለም፣ (33፥20፡ የ3፥6 ማብ ይመ፤ ዘፍ 16፥13፤ ዘኍ 12፥8፤ ሕዝ 1፥28 ይመ)። *ሰማይ፤* ሰማያዊ በሆነ የሰንፔር ቀለም ይመሰላል፤ (ሕዝ 1፥26 ይመ)።

24፥11 *እጁን አላነሣባቸውም፤* 9፥15 ይመ። *በሉ ጠጡም፤* ከቍ 3-8 የተገለጸው ቃል ኪዳን የጸና መሆኑን ለማስታወስ (ለማ መልከት) የሚበላ የቃል ኪዳን መብል ነው፤ (ከዘፍ 26፥30:31፥5 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህ መብል በክርስቶስ ሞት የጸናውን የአዲሱን ኪዳን የሚያስታውስ ቤዛ ነው፤ (1ቆሮ 11፥25-26 ይመ)።

24፥12 *በተራራው ላይ ወደ እኔ ና፤* የቍ 1ን ማብ ይመ። *የድንጋይ ጽላቶች፤* የ31፥18 ማብ ይመ። *መመሪያ፤* የቃል ኪዳን አምላክ ከሆነው ጌታ የተሰጡ መመሪያዎች በመሆ ናቸው መለኮታዊ ሕግጋት ናቸው።

24፥13 *ከረዳቱ ከኢያሱ ጋር፤* የ17፥9 ማብ ይመ።

24፥14 *ሖር፤* የ17፥10 ማብ ይመ።

24፥17 *የእግዚአብሔር ክብር፤* 16፥10 ይመ።

24፥18 *በተራራው ላይ ቈየ፤* ሙሴ የመገናኛውን ድንኳ በምን መልክ እንደሚሠራው መመሪያ እስኪቀበል ድረስ ከተራራ ው አልወረደም፤ (32፥15 ይመ)። *አርባ ቀንና አርባ ሌሊት፤* ሁለተ ኛው ሙሴ ኢየሱስ ክርስቶስ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ጾሟል፤ (ቍ 2 እና ማብ፤ ማቴ 4፥2 ይመ)።

25፥2 *ስጦታ፤* እዚህ ላይ በበጐ ፈቃደኝነት የሚደረገውን ስጦታ ያመለክታል።

25፥4 *ሰማያዊ ሐምራዊ፤ ቀይ፤* የነገሥታት ልብስ የቀ ለም ዐይነቶች ናቸው። *ሰማያዊ፣ ሐምራዊ፤* እነዚህ ቀለሞች የሚ ወሰዱት በሰሜን ምሥራቅ ሜድትራኒያን ባሕር ከሚርመሰመሱ የተለያየ ዝርያ ካላቸው ዐሳዎች ሲሆን፣ በመጀመሪያ ከነዓን ("ሐም ራዊ ምድር" ማለት ነው)፤ በኋላም ግሪኮች ፊንቄ (አሁንም "ሐም ራዊ ምድር" ማለት ነው)፤ በማለት የሰየሚት አገር ዋነኛ የኢኮ ኖሚ ምንጭ በቀለም ተነክረው ለገበያ የሚቀርቡ ልብሶች ናቸው። *ቀይ፤* በየቅጠላ ቅጠሉ ተጣብቀው ከሚኖሩ ትላ ትሎች እንቁላልና ብስባሽ የሚዘጋጅ ነው። *የበፍታ ድር፤* ዋጋው በጣም ውድ የሆነ ልብስ ሲሆን፣ (አብዛኛውን ጊዜ እንዲህ ያለውን ልብስ የሚለብሱት የግብፅ ነገሥታት ናቸው)፤ የሚዘጋጀውም ከተልባ ገለባ ተፈትሎ የሚሠራ ድር ነው። ከበፍታ ድር የሚዘጋጁ ልብሶች አብዛኛውን ጊዜ ቀለማቸው ነጫጭ በልዩ ጥበብ የሚ ሠሩ ናቸው፤ በዚህ ዐይነት የተሠሩ ልብሶች በጥንት ግብፃውያን መቃብር ውስጥ ተገኝተዋል። ልብሶቹ በልዩ ጥበብ የተሠሩና በጣም ረቂቅ በሆኑ ድሮች የተገመዱ በመሆናቸው፣ በማጉያ መነ ጽር ካልሆነ በቀር ከሐር ልብስ ለመለየት ያስቸግራል። *የፍየል ጠጕር፤* ረጃጅም ጠጕር ካላቸው ፍየሎች የሚገኝና ብዙውን ጊዜ ድን ኳን ለመሥራት የሚያገለግል ነው፤ (2ሳሙ1፥5:6፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

25፥5 *ቀይ የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ፤* የበጎቹ ጠጕር ከተ ሸለተ በኋላ ቆዳው በቀይ ቀለም ይነከራል። በዚህ መልክ የሚዘጋ ጀው ቆዳ በአሁኑ ጊዜ ለልብስና ለጫማ መሥሪያ ከሚያገለግለው ቆዳ ጋር ተመሳሳይ ነው። *ግራር፤* ከዋንዛ እንጨት የጠቆረና የጠ ነከረ ሲሆን፣ ምስጥ የማይበላው እንጨት ነው፤ ግራር በሲና ምድረ በዳ ወሽመጥ በብዛት ይገኛል።

25፥6 *ቅመሞች፤* የቅብዓ ዘይቱ ቅመሞች በ30፥23-24 ላይ ተገልጸዋል፤ እነርሱም ከርቤ፣ ቀረፋ፣ ጠጅ ሣርና ብርጉድ ናቸው። ጣፋጭ መዓዛ ላለው ዕጣን የሚሆኑት ቅመሞች በ30፥34 ላይ ተገልጸዋል፤ እነርሱም የሚንጠባጠብ ሙጫ፣ በዛጐል ውስጥ የሚገኝ ሽቶና፣ የሚሸት ሙጫ ናቸው።

የሚሆኑ መረግዶችና ሌሎች ዕንቍዎች።

[8]"ከዚያም መቅደስ እንዲሠሩልኝ አድርግ፤ እኔም በመካከላቸው አድራለሁ። [9]ማደሪያ ድንኳኑንና በውስጡ ያለውን ዕቃ ሁሉ ልክ እኔ በማሳይህ ዕቅድ መሠረት ሥሩት።

## የቃል ኪዳኑ ታቦት

25፥10-20 ተጓ ምብ - ዘፀ 37፥1-9

[10]"ርዝመቱ ሁለት ክንድ ተኩል፣ ወርዱ አንድ ክንድ ተኩል፣ ከፍታው አንድ ክንድ ተኩል የሆነ ታቦት ከግራር እንጨት[x] እንዲሠሩ አድርግ። [11]ውስጡንም ውጭውንም በንጹሕ ወርቅ ለብጠው፤ በዙሪያውም የወርቅ ክፈፍ አብጅለት። [12]አራት የወርቅ ቀለበቶች ሠርተህ ሁለቱን በአንድ በኩል ሁለቱን በሌላ በኩል ከአራቱ እግሮች ጋር አያይዝ። [13]ከዚያም መሎጊያዎችን ከግራር እንጨት ሥራ፤ በወርቅም ለብጣቸው። [14]መሎጊያዎችንም መሸከሚያ እንዲሆኑ በታቦቱ ማእዘኖች ላይ ባሉት ቀለበቶች ውስጥ አስገባቸው። [15]መሎጊያዎቹ ከታቦቱ ቀለበቶች ውስጥ ምንጊዜም መውጣት የለባቸውም። [16]የምሰጥህንም ምስክር በታቦቱ ውስጥ አኑር።

[17]"ርዝመቱ ሁለት ክንድ ተኩል፣ ወርዱ አንድ ክንድ ተኩል[ነ] የሆነ የስርየት መክደኛ[ጠ] ከንጹሕ ወርቅ ሥራለት። [18]በስርየት መክደኛው ዳርና ዳር ላይ የሚሆኑ ከወርቅ የተቀረጹ ሁለት ኪሩቤል ሥራ። [19]አንዱን ኪሩብ በአንደኛው፣ ሁለተኛውን ኪሩብ በሌላኛው ዳር አድርግ በሁለቱም ጫፎች ሁለቱን ኪሩቤል ከስርየት መክደኛው ጋር አንድ ወጥ አድርገህ ሥራቸው። [20]ኪሩቤልም ክንፎቻቸውን ወደ ላይ በመዘርጋት የስርየት መክደኛውን በክንፎቻቸው ይሸፍኑ፤ እርስ በርሳቸው ትይዩ በመሆንም ፊታቸውን ወደ ስርየት መክደኛው ያድርጉ። [21]የስርየት መክደኛውን በታቦቱ አናት ላይ አስቀምጠው፤ እኔ የምሰጥህን ምስክሩንም በታቦቱ ውስጥ አስቀምጥ። [22]በምስክሩ ታቦት ላይ ባሉት በሁለቱ ኪሩቤል መካከል፣ በስርየት መክደኛው ላይ በዚያ እኔ ከአንተ ጋር እገናኛለሁ፤ ለእስራኤላውያን የሚሆኑትን ትእዛዞቼንም እሰጥሃለሁ።

## የኅብስቱ ማስቀመጫ ጠረጴዛ

25፥23-29 ተጓ ምብ ዘፀ 37፥10-16

[23]ርዝመቱ ሁለት ክንድ፣ ወርዱ አንድ ክንድ፣ ከፍታው አንድ ክንድ ተኩል[ጮ] የሆነ ጠረጴዛ ከግራር እንጨት ሥራ። [24]በንጹሕ ወርቅ ለብጠው፤ በዙሪያውም የወርቅ ክፈፍ አድርግለት። [25]ዙሪያውንም አንድ ስንዝር[ኣ] ስፋት ያለው ጠርዝ አብጅለት፤ በጠርዙም ዙሪያ የወርቅ ክፈፍ አድርግለት። [26]ለጠረጴዛው አራት የወርቅ ቀለበቶች ሠርተህ፣ አራቱ እግሮች ባሉበት በአራቱ ማእዘኖች ላይ አያይዛቸው። [27]ጠረጴዛውን ለመሸከም የሚያገለግሉትን መሎጊያዎች ይይዙ ዘንድ፣ ቀለበቶቹ ከክፈፉ አጠገብ ይሁኑ። [28]መሎጊያ

25፥7 ዘፀ28፥4፡ 6-4፤29፥5፤ መሳ8፥27፤ ሆሴ3፥4፤ዘሌ8፥8
25፥8 ዘፀ 29፥45፤ 36፥1-5፤ዘሌ4፥6፤ 10፥4፡7፤21፥12፡23፤ 26፥11-12፤ዘኍ 3፥28፤5፥3፤ዘዳ12፥11፤ 1ነገ6፥13፤ዕካ2፥10፤ 2ቆሮ6፥16፤ዕብ9፥1-2
25፥9 ቍ40፤ ዘፀ 26፥30፤27፥8፤31፥11 ፤39፥32፡42፡43፤ዘኍ 8፥4፤1ዜና28፥11፡ 19፤ ሐሥ7፥44፤ዕብ 8፥5
25፥10 ዘዳ10፥1-5 ፤1ነገ6፥19፤ዕብ9፥4
25፥11 ቍ24፤ ዘፀ30፥3
25፥12 ቍ26፤ ዘፀ30፥4
25፥13 ቍ28፤ ዘፀ27፥6፤30፥5፤ 37፥28
25፥14 ዘፀ27፥7፤ 40፥20፤1ዜና15፥15
25፥15 1ነገ8፥8
25፥16 ዘፀ16፥34፤ ዕብ9፥4
25፥17 ቍ21፤ዘሌ 16፥13፤ ሮሜ3፥25
25፥18 ዘፀ26፥1፡ 31፤36፥35፤1ነገ6፥ 23፡27፤8፥6፤2ዜና3፥ 10-13፤ዕብ9፥5
25፥20 ዘፍ3፥24፤ ዘፀ37፥9፤1ነገ8፥7፤ 1ዜና28፥18፤ዕብ9፥5
25፥21 ቍ10-15፤ ዘፀ16፥34፤26፥34፤ 40፥20፤ዘዳ10፥5፤ ዕብ9፥4
25፥22 ዘፀ19፥3፤29፥42፤30፥6፡36፤ዘሌ1፥1፤16፥2፤ዘኍ 7፥89፤17፥4፤1ሳሙ4፥4፤2ሳሙ6፥2፤22፥11፤2ነገ19፥15፤1ዜና13፥6፤ 28፥18፤መዝ18፥10፤80፥1፤99፥1፤ኢሳ37፥16፤ኤር3፥16
25፥23 ቍ30፤ዘፀ26፥35፤40፥4፡22፤ዘሌ24፥6፤ዘኍ3፥31፤1ነገ7፥48፤ 1ዜና28፥16፤2ዜና4፥8፡19፤ሕዝ41፥22፤44፥16፤ዕብ9፥2

[x]10 ርዝመቱ 1.1 ሜትር፣ ጐኑና ርዝመቱ 0.7 ሜትር ያህል ነው።
[ነ]17 ርዝመቱ 1.1 ሜትር፣ ጐኑና ርዝመቱ 0.7 ሜትር ያህል ነው።
[ጠ]17 በትውፊት፣ *የጸጋው ዙፋን* በመባል ይታወቃል።
[ጮ]23 ርዝመቱ 0.9 ሜትር፣ ጐኑና 0.5 ርዝመቱ 0.7 ሜትር ያህል ነው
[ኣ]25 ወደ 8 ሳንቲ ሜትር ያህል ነው።

25፥7 *ሌሎች ዕንቍዎች፤* 28፥17-20 ይመ።

25፥8 *መቅደስ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "የተቀደሰ ቦታ" ወይም "የተለየ ስፍራ" ማለት ነው፤ የ3፥5 ማብ ይመ።

25፥9 *ማደሪያ ድንኳን፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ማደሪያ ቦታ" ማለት ነው። ይህ ቃል ሰዎች የሚኖሩበትን ቦታ ለማመልከት የገባው በጣም በጥቂቱ ነው፤ ሁልጊዜ ማለት ይቻላል ቃሉ የሚያመለክተው እግዚአብሔር በሕዝቡ መካከል የሚኖርበትን ቦታ ነው፤ (ቍ 8፤ 29፥45-46፤ ዘሌ 26፥11፤ ሕዝ 37፥27፤ ከዮሐ 1፥14፤ ራእ 21፥3 ጋር ያነጻጽር)። *ዕቅድ፤* የቍ 40 ማብ ይመ።

25፥10 *ታቦት፤* ቍ 14 ይመ። በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከሚገኙት ዕቃዎች መካከል ታቦቱ በመጀመሪያ የተጠቀሰው፣ በሕዝቡ መካከል ለመኖር የወደደውን (ቍ 9 ማብ ይመ) የታላቁን ንጉሥና ጌታ ዙፋን ለማመልከት ነው፤ (1ሳሙ 4፥4፤ 2ሳሙ 6፥2 ይመ)።

25፥11 *በንጹሕ ወርቅ፤* ከብርና ከሌሎች ብረታ ብረቶች ጋር ያልተደባለቀ ማለት ነው።

25፥12 *ቀለበቶች፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ቤቶች" ማለት ሲሆን የታቦቱ መሸከሚያ መሎጊያዎች የሚገቡበት ነው፤ (ቍ 14 ይመ)።

25፥16 *ምስክር፤* የሲና ቃል ኪዳን ሕግጋት የሆኑት ዐሥርቱ ትእዛዛት የተጻፉት ሁለቱ ጽላቶች ማለት ነው፤ (20፥1-17፡ 31፥18 ይመ)። ምስክር ለሚለው ቃል የገባው የዕብራይስጡ ቃል "የቃል ኪዳን ሕግጋት" ከሚለው ከባቢሎናውያን ቃል ጋር ይዛመዳል፤ (የቍ 22 እና የ16፥34 ማብ ይመ)።

25፥17 *ስርየት፤* እርቅ ማለት ሲሆን፣ ከእርሱ ተለይተው የነበሩትን እግዚአብሔር በጸጋው ከራሱ ጋር "አንድ" ለማድረግ ወደ ራሱ የሚስብበትን ሁኔታ ይገልጻል። በብሉይ ኪዳን የሕዝቡን ኀጢአት ለማንጻት የሚፈሰው ደም ስርየትን ያስገኛል፤ (ዘሌ 17፥1 እና ማብ ይመ)፤ በአዲስ ኪዳን ደግሞ አንድ ጊዜ የፈሰሰው የኢየሱስ ክርስቶስ ደም እንዲሁ የኀጢአትን ስርየት ያስገኛል፤ (ሮሜ 3፥25፤ 1ዮሐ 2፥2 ይመ)። *የስርየት መክደኛ፤* ዘሌ 12፥2 እና ማብ ይመ። የእግዚአብሔር ዙፋን ምሳሌ የሆነው ታቦት በዚህ በስርየት መክደኛ ይሸፈናል፤ ይህም እግዚአብሔር ለሕዝቡ ያለውን ምሕረት ያሳያል፤ እንግዲህ መከበርና መፈራት የሚገባው እንዲህ ያለው አምላክ ብቻ ነው፤ (መዝ130፥3-4 ይመ)።

25፥18 *ኪሩቤል፤* ምናልባት በብዙ የጥንት መካከለኛው ምሥራቅ አካባቢዎች (የዘፍ 3፥24 ማብ ይመ) የሚኖሩ ነገሥታት ዙፋኖቻቸውን ለማስጌጥ በእጅ መደገፊያዎች ላይ ከሚያስቀርጿቸውና ግማሽ አካላቸው የአንበሳ ግማሽ አካላቸው ደግሞ የሰው መልክ ካላቸው የጥንት ግብፃውያን ባለ ክንፍ ሐውልቶች ጋር ሳይመሳሰሉ አይቀሩም (የቍ 10 ማብ ይመ)። በብሉይ ኪዳን ኪሩቤል በምድር የእግዚአብሔርን መኖርያ የሚጠብቁ ምሳሌዎች ናቸው፤ (1ሳሙ 4፥4፤ 2ሳሙ 6፥2፤ 2ነገ 19፥15፤ መዝ 99፥1 ይመ)። ከታቦቱ መክደኛ ላይ ሆኖ (የእግዚአብሔር ዙፋን ምሳሌ ነው)፤ እግዚአብሔር ለሙሴ መመሪያን ይሰጠው ነበር፤ (ቍ 22፤ ዘኍ 7፥89 ይመ)። ታቦቱ በኢየሩሳሌም በሚገኘው ቤተ መቅደስ ውስጥ እንዲቀመጥ በመደረጉ ኢየሩሳሌም የእግዚአብሔር መኖሪያ ከተማ ሆነች፤ (መዝ 9፥11፤ 18፥10 እና ማብ ይመ)።

25፥22 *በምስክሩ ታቦት፤* እንዲህ የሚል ስም የተሰጠው ምስክሩን የያዙት ጽላቶች የሚገኙት በታቦቱ ውስጥ በመሆኑ ነው (የቍ16 ማብ ይመ)። "በምስክሩ ታቦት" የሚለው ሐረግ "በቃል ኪዳኑ ታቦት" ከሚለው የተለመደ ሐረግ ጋር ተመሳሳይ ነው፤ (ዘኍ 10፥33 ይመ)። *እገናኛለሁ፤* የ23፥21 ማብ ይመ።

25፥23 *ጠረጴዛ፤* ይህ ለሁለተኛ ጊዜ ከተሠራው ቤተ መቅደስ ውስጥ (ቤተ መቅደሱ የተሠራው በዘሩባቤል ነው)፤ በአንታያከስ ኤፒፋነስ የተወሰደው ጠረጴዛ ምስል በቲቶ ሐውልት ቅስት ላይ ከሌሎች ዕቃዎች ጋር የተቀረጸ ሲሆን፣ እነዚህ ዕቃዎች ሮማውያን ኢየሩሳሌምን 70 ዓ.ም ላይ ድል ሲያደርጉ የተወሰዱ ናቸው።

25፥26 *ቀለበቶች፤* የቍ 12 ማብ ይመ።

ዎቹን ከግራር እንጨት ሥራቸው፤ በወርቅ ለብጣቸው፤ ጠረጴዛውንም ተሸከምባቸው:: [29]ለመጠጥ ቍርባን መፍሰሻ ይሆኑም ዘንድ ዝርግ ሳሕኖችንና ወጭቶችን፣ እንዲሁም ማንቆርቆሪያዎቹንና ጎድጓዳ ሳሕኖቹን ከንጹሕ ወርቅ ሥራቸው:: [30]በማንኛውም ጊዜ በፊቴ እንዲሆን ኅብስተ ገጹን በዚህ ጠረጴዛ ላይ አስቀምጥ::

### የመብራቱ መቅረዝ

25፥31-39 ተጓ ምብ - ዘፀ 37 17-24

[31]ከንጹሕ ወርቅ መቅረዝ ሥራ፤ መቆሚያና ዘንግ አብጅለት፤ ጽዋ መሰል አበባዎች፤ እንቡጦችና የፈነዱ አበባዎች ከመቅረዙ ጋር ወጥ ሆነው ይሠሩ:: [32]ከመቅረዙ ግራና ቀኝ ጎን ጋር የተያያዙ፣ በአንዱ በኩል ሦስት በሌላው በኩል ሦስት በድምሩ ስድስት ቅርንጫፎች ይኑሩት:: [33]ከመቅረዙ ጋር የተያያዙት ስድስቱ ቅርንጫፎች እያንዳንዳቸው እንቡጥና ቀንበጥ ያሏቸው የለውዝ አበባ ቅርጽ ካሏቸው ሦስት ጽዋ መሰል አበባዎች ጋር ያኑሯቸው:: [34]በመቅረዙም ላይ አበባዎች እንቡጥና ቀንበጥ ያሏቸው አራት የለውዝ አበባ ቅርጽ ያሏቸው ጽዋዎች ይኑሩ:: [35]በመቅረዙ ላይ ላሉት ለስድስቱ ቅርንጫፎች እንቡጥ በመጀመሪያዎቹ ጥንድ ቅርንጫፎች ሥር፣ ሁለተኛውም እንቡጥ በሁለተኛው ጥንድ ሥር፣ ሦስተኛውም እንቡጥ በሦስተኛው ጥንድ ሥር ይሁን:: [36]ዕንቡጦቹና ቅርንጫፎቹ ሁሉ ከመቅረዙ ጋር አንድ ወጥ ሆነው ከንጹሕ ወርቅ ተቀርጸው ይሠሩ::

[37]"ከዚያም ሰባት መብራቶች ሠርተህ ከመቅረዙ ፊት ለፊት ለሚገኘው ስፍራ ብርሃን እንዲሰጡ ከመቅረዙ ላይ አስቀምጣቸው:: [38]መኰስተሪያና የኵስታሪ ማስቀመጫ ሳህኖቹም ከንጹሕ ወርቅ ይሠሩ:: [39]ለመቅረዙና ለዕቃዎቹ ሁሉ የሚያስፈልገው አንድ መክሊት ንጹሕ ወርቅ ነው:: [40]በተራራው ላይ ባሳየሁህ ዕቅድ መሠረት መሥራትህን ልብ በል::

25፥28 ቍ13
25፥29 ዘኍ4፥7
25፥30 ዘፀ35፥13፤ 39፥36፤40፥4:23፤ዘሌ 24፥5-9፤ዘኍ4፥7፤ 1ሳሙ21፥4-6፤1ነገ 7፥48፤1ዜና23፥29
25፥31 ዘፀ26፥35፤ 31፥8፤35፥14፤39፥37 ፤40፥4:24፤ዘሌ24፥4፤ ዘኍ3፥31፤1ነገ7፥49፤ 2ዜና4፥7፤ዘካ4፥2፤ዕብ9፥2፤ራእ1፥12
25፥36 ቍ18፤ ዘኍ8፥4
25፥37 ዘፀ27፥21፤ 30፥8፤ዘሌ24፤3-4፤ዘኍ8፥2፤ 1ሳሙ3፥3፤ 2ዜና13፥11
25፥38 ቍ37፤ ዘኍ4፥9
25፥40 ቍ9፤ ሐሥ7፥44፤ዕብ8፥5
26፥1 ዘፀ25፥18፤ 29፥42፤40፥2፤ ዘሌ8፥10፤ዘኍ1፥50፤ ኢሱ22፥19:29፤ 2ሳሙ7፥2፤ 1ነገ1፥39፤ ሐሥ7፥44፤ዕብ8፥2: 5፤13፥10፤ራእ21፥3፤
26፥2 ቍ8
26፥6 ቍ11
26፥8 ቍ2
26፥11 ቍ6

### የማደሪያው ድንኳን

26፥1-37 ተጓ ምብ - ዘፀ 36፥8-38

**26** "በቀጭኑ ከተፈተለ የበፍታ ድርና በሰማያዊ፣ በሐምራዊና በቀይ ማግ በተሠሩ ዐሥር መጋረጃዎች ማደሪያ ድንኳኑን ሥራ፤ እጀ ብልኅ ሠራተኛም ኪሩቤልን ይጥለፍባቸው:: [2]መጋረጃዎች ሁሉ እኩል ይሁኑ፤ የእያንዳንዱ መጋረጃ ርዝመት ሃያ ስምንት ክንድ ወርዱም አራት ክንድ[*] ይሁን:: [3]አምስቱን መጋረጃዎች አገጣጥመህ ስፋ፤ የቀሩትንም አምስት መጋረጃዎች እንደዚሁ አገጣጥመህ ስፋቸው:: [4]ከዳር በኩል ባለው መጋረጃ ጠርዝ ላይ፣ ከሰማያዊ ጨርቅ የተሠሩ ቀለበቶች አድርግ፤ በሌላውም የመጋረጃ ጠርዝ ላይ እንዲሁ አድርግ:: [5]ቀለበቶችን ትይዩ በማድረግ አምሳ ቀለበቶችን በአንደኛው ጠርዝ መጋረጃ፣ አምሳ ቀለበቶችንም በሌላው ጠርዝ መጋረጃ አድርግ:: [6]ከዚያም የመገናኛው ድንኳን አንድ ወጥ ይሆን ዘንድ መጋረጃዎቹን በአንድ ላይ ለማያያዝ አምሳ የወርቅ ማያያዣዎችን ሥራ::

[7]"ማደሪያ ድንኳኑን ከላይ ሆነው የሚሸፍኑ ዐሥራ አንድ የፍየል ጠጕር መጋረጃዎች ሥራ:: [8]ዐሥራ አንዱም መጋረጃዎች እኩል ይሁኑ፤ የእያንዳንዱ ርዝመት ሠላሳ ክንድ ወርዱም አራት ክንድ[*] ይሁን:: [9]አምስቱን መጋረጃዎች በአንድ ላይ፣ እንደዚሁም ስድስቱን መጋረጃዎች በአንድ ላይ አድርገህ ስፋቸው፤ ከማደሪያው ድንኳን ፊት ለፊት ስድስተኛውን መጋረጃ እጠፍና በላዩ ላይ ደርበው:: [10]በአንድ በኩል ባለው መጨረሻ መጋረጃ ጠርዝ ላይ አምሳ ቀለበቶችን፣ እንዲሁም በሌላ በኩል ባለው መጨረሻ መጋረጃ ጠርዝ ላይ አምሳ ቀለበቶችን አድርግ:: [11]ከዚያም አምሳ የናስ ማያያዣዎችን ሥራ፤ ድንኳኑን አንድ ወጥ አድርጎ ለማያያዝ በቀለበቶቹ ውስጥ ጨምራቸው:: [12]ስለ

*2 ርዝመቱ 12.5 ሜትር ወርዱ 1.8 ሜትር ያህል ነው::
*8 ርዝመቱ 13.5 ሜትር ወርዱ 1.8 ሜትር ያህል ነው::

25፥30 *ኅብስት፤* ኅብስተ ገጽ የተባለውም በእግዚአብሔር ፊት የሚቀርብ ኅብስት በመሆኑ ነው፤ (በ33፥14-15 እና በኢሳ 63፥9 ላይ እንደተመለከተው):: ይህ ኅብስት (በቍጥር ዐሥራ ሁለት ሲሆን፣ ለእያንዳንዱ ነገድ አንድ ይደርሳል)፤ ለእግዚአብሔር የሚሰጠውን ሕያው ኅብስት የሚያመለክት ሲሆን፣ ይህም እስራኤል የድካሟን ፍሬ ለእግዚአብሔር እንደለየ ችና (እንደቀደሰችና) እንዲህ ያለውንም ፍሬ ያገኘችው ከእግዚአብሔር በረከት የተነሣ ብቻ እንደ ሆነ ያሳያል፤ (ዘሌ24፥5-9 ይመ)::

25፥31 *ጽዋ መሰል አበባዎች፤ እንቡጦችና የፈነዱ አበባዎች፤* የመቅረዙ ንድፍ የተወሰደው በመካከለኛው ምሥራቅ በፀደዩ ወራት ከሌሎች ዛፎች ሁሉ ቀድሞ ከሚያብበው የለውዝ አበባ ቅርጽ አበባ አቃፊዎቹን (የአበባውን ውጫዊ ሽፋን) ወይም የለውዝ ፍሬዎቹን ይመስላሉ::

25፥37 *ሰባት፤* ፍጹምነትን ያመለክታል:: *መብራቶች፤* የጥንት መብራቶች መጠናቸው አነስተኛ ቅርጻቸው ደግሞ ጐድጓዳ ሲሆን፣ የሚሠሩትም ከሸክላ ነው:: ሰባት ጡት ያላቸው መብራቶች ከሙሴ ዘመን ጀምሮ እንደነበሩ ተረጋግጧል:: በቤት ሻን እና በመጊዶ ፍርስራሾች ሥር ከብረት የተሠሩ መብራቶች ተገኝተዋል:: ሆኖም የቤተ መቅደሱን ዓይነት የሚመስሉ መብራቶች የነበሩት በታላቁ ሄሮድስ ዘመን ሲሆን፣ እነዚህ መብራቶች በሮም በቲቶ ሐውልት ቅስት ላይ ተቀርጸው ይታያሉ:: መብራቶቹ ሌሊቱን ሙሉ መብራት ያለባቸው ሲሆን፣ ይህንንም የሚቆጣጠሩት ካህናት ናቸው:: ለመብራቶቹ የሚያስፈልገውን ዘይት ሕዝቡ ያቀርብ ነበር:: ከመብራቶቹ የሚወጣው ብርሃን ራሳቸውን ለእግዚአብሔር በለዩት በእስራኤላውያን ሕይወት የሚንጸባረቀውን የእግዚአብሔርን ክብር ይወክላል፤ (29፥43):: 27፥20-21 ይመ::

*25፥40፤* ይህ ጥቅስ "ጥላ ወይም ምሳሌ" የሆነውን ነገር (የብሉይ ኪዳኑን ውጫዊ ሥርዐት) እውነተኛ ከሆነው (ከአዲስ ኪዳኑ ክርስቶስ) ጋር ለማነጻጸር በዕብ 8፥5 ላይ ተጠቅሶአል:: ዕብ 10፥1 ይመ::

26፥1 *ማደሪያ፤* የ25፥9 ማብ ይመ:: የማደሪያው ድንኳን መሠረታዊ አወቃቀር ርዝመቱ አራት ሜትር ከአምሳ ሳንቲ ሜትር፣ የጐኑ ስፋት ዐሥራ ሦስት ሜትር ከሰባ ሳንቲ ሜትር፣ ቁመቱ ደግሞ አራት ሜትር ከኀምሳ ሳንቲ ሜትር ነው:: በቀጭኑ ከተፈተለ የበፍታ ድር የተዘጋጀው መጋረጃ (ቍ1-6) ከፍየል ጠጕር በተሠራና (ቍ7-13) በሌሎች ሁለት ቆዳዎች፣ አንደኛው ቀይ ቀለም የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ፣ ሁለተኛው ደግሞ የተለፋ የአቆስጣ ቈዳ መደረብ አለበት (ቍ 14):: የማደሪያው ድንኳን የውስጥ ጣራ ምናልባት ዝርግ ሳይሆን አይቀርም፤ ሆኖም ከውስጥ በኩል ጣራውን የሚሸፍነው ቆዳ እንደ ድንኳን ያለ ቅርጽ ያለ ቅርጽ ይኑረው፣ አይኑረው አይታወቅም:: ማደሪያው የእግዚአብሔር ንጉሣዊ ድንኳን ምሳሌ ነው:: *በቀጭኑ ከተፈተለ የበፍታ ድርና በሰማያዊ፣ በሐምራዊና በቀይ ማግ፤* የ25፥4 ማብ ይመ:: *ኪሩቤል፤* ንጉሣዊ መኖሪያውን ያመለክታል (25፥18 እና ማብ ይመ)::

ድንኳኑ መጋረጃዎች ትርፍ ቁመትም፣ ትርፍ ግማሽ መጋረጃ ከማደሪያው ድንኳን ጀርባ ላይ እንዲንጠለጠል ይሁን። [13]የድንኳኑ መጋረጃዎች በሁለቱም ጐኖች አንድ ክንድ ርዝመትᐟ ይኖራቸዋል፤ የተረፈውም የማደሪያውን ድንኳን ጎኖች እንዲሸፍን ሆኖ ይንጠለጠላል፤ [14]ለድንኳኑ በቀይ ቀለም የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ ልብስ አብጅ፤ በላዩም ላይ የአቆስጣ ቆዳ ይሁንᵀ።

[15]"ለማደሪያው ድንኳን ከግራር እንጨት ወጋግራዎችን አብጅ። [16]እያንዳንዱም ወጋግራ ርዝመቱ ዐሥር ክንድ ወርዱም አንድ ክንድ ተኩልᵘ ይሁን፤ [17]ሁለት ጉጦችም ጎን ለጎን ይሁኑለት፤ የማደሪያውን ድንኳን ወጋግራዎች ሁሉ በዚሁ መልክ አብጅ [18]ለማደሪያው ድንኳን ክፍል ሃያ ወጋግራዎችን ሥራ። [19]ከሥራቸው የሚሆኑ አርባ የብር መቆሚያዎችን አብጅ፤ በእያንዳንዱ ጉጠት ሥር አንድ መቆሚያ ሲሆን፣ ለእያንዳንዱም ወጋግራ ሁለት መቆሚያዎች ይኑሩ። [20]በሌላው ጎን፣ ከማደሪያው ድንኳን በስተ ሰሜን በኩል ሃያ ወጋግራዎችን አብጅ፤ [21]በእያንዳንዱም ወጋግራ ሥር ሁለት ሁለት መቆሚያ ሆኖ አርባ የብር መቆሚያዎችን አብጅ። [22]በዳር በኩል ለሚገኘው ይኸውም በምዕራብ ጠርዝ ላለው የማደሪያው ድንኳን ስድስት ወጋግራዎች አብጅ። [23]ዳርና ዳር ላሉት ማእዘኖች ሁለት ወጋግራዎች አብጅ። [24]በእነዚህ ሁለት ማእዘኖች ላይ ከታች እስከ ላይ ድረስ ድርብ ሲሆኑ በአንድ ቀለበት ውስጥ የሚገጥሙ መሆን አለባቸው፤ በሁለቱም ወገን እንዲሁ መሆን አለበት። [25]ስለዚህ ስምንት ወጋግራዎች አሉ፤ እንዲሁም ዐሥራ ስድስት የብር መቆሚያዎች ሲኖሩ፣ ለእያንዳንዱ ወጋግራ ሁለት ሁለት መቆሚያ ይሆናል።

[26]"ደግሞም ከግራር ዕንጨት አግዳሚዎችን አብጅ፤ በአንድ በኩል ላሉት የማደሪያው ድንኳን ወጋግራዎች አምስት፣ [27]በሌላው ጎን ላሉት አምስት፣ በማደሪያው ድንኳን ዳር በምዕራብ በኩል ባሉት ወጋግራዎች አምስት አብጅ። [28]መካከለኛው አግዳሚ በወጋግራዎቹ መካከል ከጫፍ እስከ ጫፍ ይተላለፍ። [29]ወጋግራዎቹን በወርቅ ለብጣቸው፤ አግዳሚዎቹን ለመያዝ የወርቅ ቀለበቶች አብጅ፤ አግዳሚዎቹንም በወርቅ ለብጣቸው።

26፥14 ዘኍ3፥25፤ 4፥25
26፥19 ቍ21፡25፡ 32፤ዘፀ38፥27
26፥21 ቍ19

ᐟ13 ርዝመቱ 0.5 ሜትር ያህል ነው።
ᵀ14 ይህ የባሕር እውሬ ነው።
ᵘ16 ርዝመቱ 4.5 ሜትር፣ ወርዱ 0.7 ሜትር ያህል ነው።

26፥14 *በቀይ ቀለም የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ ... የአቆስጣ ቆዳ፤* የ25፥5 ማብ ይመ።

26፥17 *ጉጦች፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "እጆች" ማለት ሲሆን፣ ምናልባት ከእያንዳንዱ ጣንቃ ታች የሚገኙና ከአቃፊዎቹ ጋር የሚጋጠሙ ናቸው (ቍ 19)።

26፥19 *አርባ የብር መቆሚያዎች፤* እነዚህ እንዲሁም በቍ 21 ላይ ያሉት አርባ፣ በቍ 25 ላይ ያሉት አስራ ስድስትና እና በቍ 32 ላይ ያሉት አራት አንድ ላይ ሲደመሩ፣ አንድ መቶ እግሮች ይሆናሉ፤ እነዚህም ከእያንዳንዱ የእስራኤል ማኅበር የተሰበሰቡ የብር መክሊቶች ናቸው፤ (38፥27 ይመ)።

26፥23 *ማዕዘኖች፤* ምናልባት ጣንቃዎቹ የተጋጠሙባቸውን ማዕዘኖች ሊሆን ይችላል።

26፥26 *አግዳሚዎች፤* በሰሜን፣ በደቡብ፣ በምዕራብ ጉን ያሉትን የአደባባዩን ወጋግራዎች የሚያጠናክሩ ናቸው።

26፥29 *ቀለበቶች፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ቤቶች" ማለት ነው፤ (የ25፥12 ማብ ይመ)።




በምድረ በዳ በሙሴ አማካይነት የተሰጠው አዲስ የሃይማኖት ትምህርት ከመገናኛው ድንኳን ጋር በተያያዙ ሥርዓቶች ላይ ያማከለና የእስራኤልን መሰየት መንግሥትና በያህዌ ጌትነት ሥር አንድ መሆን አጉልቶ የሚያሳይ ነው።

ጥቂት የአምልኮ እቃዎች በሲና ተገኝተዋል፤ እነርሱም የግብፅ አምልኮ ነፀብራቅ ይታይባቸዋል።

ተንቀሳቃሽ የሆኑ በዘንግ ተይዘው የሚሄዱና በስስ ወርቅ የተለበጡ የአምልኮ እቃዎች በጥንታዊቷ የግብፅ መንግሥት ነበሩ። 2800-2250 ዓ.ቅ.ክ በተለይም በ18ኛና በ19ኛ የግብፅ ሥርወ መንግሥታት ጎልቶ የሚታይ ነው (1570-1180)።

የእነዚህ እቃዎች አሠራር በዘፀአት 25-40 ካሉት ዝርዝሮች ጋር ሲነጻጸር ተመሳሳይነት አለው። የተሠሩበት ዘመንም (የናስ ዘመን መገባደጃ) ሙሴ ከነበረበት ዘመን ጋር አንድ ነው።

[30]"ማደሪያ ድንኳኑንም በተራራው ላይ ባየኸው ዕቅድ መሠረት ትከለው።
[31]"ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ መጋረጃ አብጅ፤ እጀ ብልህ ሠራተኛም ኪሩቤልን ይጥለፍበት። [32]በወርቅ በተለበጡ ከግራር እንጨት በተሠሩና በአራቱ የብር መቆሚያዎች ላይ በቆሙት በአራቱ ምሰሶዎች፣ በወርቅ ኰላቦች ላይ አንጠልጥለው። [33]መጋረጃውን በማያያዣዎቹ ላይ ስቀለው፤ የምስክሩንም ታቦት ከመጋረጃው በስተኋላ አስቀምጠው፤ መጋረጃውም መቅደሱን ከቅድስተ ቅዱሳኑ ይለያል። [34]በቅድስተ ቅዱሳኑ ውስጥ በምስክሩ ታቦት ላይ የማስተስረያውን ክዳን አስቀምጥ። [35]ጠረጴዛውን ከመገናኛው ድንኳን በስሜን በኩል ከመጋረጃው ውስጥ አስቀምጠው፤ መቅረዙንም ከእርሱ ትይዩ በማድረግ በደቡብ በኩል አድርገው።
[36]"ለድንኳኑ ደጃፍ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ በጥልፍ ዐዋቂ የተጠለፈ መጋረጃ አብጅ። [37]ለዚህም መጋረጃ የወርቅ ኰላቦችንና ከግራር እንጨት የተሠሩ፣ በወርቅ የተለበጡ አምስት ምሰሶዎችን አብጅ፤ አምስት የናስ መቆሚያዎችንም አብጅላቸው።

26፥30 ዘፀ25፥9፤ 40፥2፤ሥራ7፥44፤ ዕብ8፥5
26፥31 ዘፀ25፥18፤ ዘኍ4፥5፤2ዜና3፥14፤ ማቴ27፥51፤ ሉቃ23፥45፤ዕብ9፥3
26፥32 ቍ 19
26፥33 ዘፀ27፥21፤ 35፥12፤40፥3:21፤ ዘሌ16፥2:16፤ዘኍ 3፥31፤4፥5፤1ነገ6፥16 17፥50፤8፥6፤2ዜና 3፥8:14፤5፥7፤ሕዝ 41፥4፤ዕብ9፥2-3
26፥34 ዘፀ25፥21፤ 30፥6፤37፥6፤ ዘሌ16፥2፤ዕብ9፥5
26፥35 ዘፀ 25፥23: 31፤ዕብ9፥2
26፥36 ዘፀ35፥15፤40፥5:28፤መዝ45፥14፤ሕዝ16፥10፤26፥16፤27፥7

26፥30 *ዕቅድ፤* የ25፥40 ማብ ይመ።
*26፥31-35፤* መጋረጃው ማደሪያውን ሁለት ቦታ ይከፍላል፤ ይኸውም ቅድስትና ቅድስተ ቅዱሳኑ ናቸው፤ የመጀመሪያው ሁለተኛውን እጥፍ ይበልጠዋል። ቅድስተ ቅዱሳኑ ርዝመቱ አራት ሜትር ከኀምሳ ሳንቲ ሜትር፣ የጐኑ ስፋት አራት ሜትር ከኀምሳ ሰባት ሳንቲ ሜትር፣ ከፍታው አራት ሜት ከኀምሳ ሰባት ሳንቲ ሜትር ሲሆን፣ ከበፍታ በተሠራ መጋረጃ የተጋረደና በውስጡም የምስክሩን ታቦት ብቻ ይዞ ይገኛል፤ ይህ ክፍል የእግዚአብሔር ዙፋን ያለበትን ክፍል ይወክላል። ቅድስቱ ደግሞ የንጉሡ እንግዶች በገጸ ኅብስቱ፣ (የ25፥30 ማብ ይመ)፣ ከመቅረዙ በሚወጣው ብርሃን (የ25፥37 ማብ ይመ) እና ከዕጣን መሠዊያው በሚወጣው መዓዛ መመስላቸውን ይወክላል (የ30፥1 ማብ ይመ)።
26፥31 *መጋረጃ፤* ይህ መጋረጃ ቅድስቱን ከቅድስተ ቅዱሳኑ ለመለየት ያገለግላል፤ (ቍ 33 ይመ)፤ *ታቦቱን ስለሚሸፍን* (27፥31:የ16፥34 እና የ25፥22 ማብ ይመ)፣ የሚሸፍን መጋረጃ ተብሎ ይጠራል፤ (39፥34: 40፥21፤ ዘኍ 4፥5 ይመ)። ክርስቶስ በሞተ ጊዜ ሄሮድስ ያሠራው ቤተ መቅደስ መጋረጃ ተቀዶ ለሁለት በመከፈሉ አማኞች ወደ እግዚአብሔር ለመቅረብ ችለዋል፤ (ማር 15፥38፤ ዕብ 6፥19-20: 10፥19-22 ይመ)። *ኪሩቤል፤* ቍ 1 እና ማብ ይመ፤ ወደ ቅድስት በሚያስገባው መግቢያ ላይ ያለው መጋረጃ ኪሩቤል የለውም፤ (ቍ 36)።
26፥37 *ናስ፤* በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ያሉት ዕቃዎች የተሠሩት ከወርቅ ሲሆን፣ ድንኳኑን ከውጭ በኩል የሚሸፍነው መጋርጃ ከሚንጠለጠልበት ባልእግር ምሰሶ ጀምሮ በናስ የተሠሩ ናቸው፤ (ቍ 36 ይመ)። ለእግዚአብሔር ማደሪያ ድንኳን ቀረብ ብለው የሚገኙት ዕቃዎች የተሠሩት ወይም የተለበጡት ከወርቅ ሲሆን ከማደሪያው ራቅ ብሎ ሲኼድ የሚገኙት ዕቃዎች ደግሞ የተሠሩት ወይም የተለበጡት ከነሐስ ነው፤ (27፥2-6፤ 30፥18 ይመ)። የድንኳኑን ካንቃዎች የደገፉት ካንካዎችና መጋረጃውያን የሚይዙት አራቱ ምሰሶዎች የተሠሩት ከብር ነው፤ (ቍ 19:21: 25:32 ይመ)።

## የመገናኛው ድንኳን እቃዎች

የእግዚአብሔር የመዋጀት ኪዳን ለሚያመልከው ሰው እያንዳንዱን እቃ የትምህርት መሣሪያ በማድረግ በድንኳኑ ውስጥ የተቀመጠ ነው። የሌዋውያን ቀሳውስት የግብጻውያንን ስም ምናልባትም ልምምዳቸውን በመጨመር፣ ስለ ታቦቱ ግልጽ የሆነ ትኩረት ሰጥተውታል። ዝርዝር የአሠራር መንገዶችና መስፈርቶች ግልጽ ሆነው በዘጸአት 25-40 ባለው ክፍል ስለተቀመጡ እነዚህን እቃዎች እንደገና ለመሥራት ይቻላል።



## የሚቃጠል መሥዋዕት ማቅረቢያ መሠዊያ

27፥1-8 ተጓ ምብ - ዘፀ 38፥1-7

**27** "ከፍታው ሦስት ክንድ[ሀ] የሆነ መሠዊያ ከግራር እንጨት ሥራ፤ ርዝመቱ አምስት፣ ስፋቱም አምስት ክንድ ሆኖ ባለ አራት ማእዘን[ለ] ይሁን። [2]ቀንዶቹና መሠዊያው አንድ ወጥ ይሆኑ ዘንድ በአራቱም ማእዘኖች ላይ ቀንድ አድርግለት፤ መሠዊያውንም በነሐስ ለብጠው። [3]ዕቃዎቹን ሁሉ ይኸውም የዐመድ ማስወገጃ ምንቸቶችን፣ መጫሪያዎችን፣ ጐድጓዳ ሳሕኖችን፣ ሜንጦዎችንና የፍም መያዣዎችን ከናስ አብጃቸው። [4]ዐመድ ማውረጃ የሚሆን እንደ መረብ የሆነ የናስ ፍርግርግ አድርግለት በአራቱም የመረብ ማእዘኖች ላይ የነሐስ ቀለበቶች አብጅ። [5]እስከ መሠዊያው ወገብ እንዲደርስ በመሠዊያው ዙሪያ ባለው እርከን ሥር አድርገው። [6]የግራር ዕንጨት መሎጊያዎችን ለመሠዊያው ሠርተህ በነሐስ ለብጣቸው። [7]በሸክም ጊዜ በመሠዊያው ሁለቱም ጎኖች እንዲሆኑ፣ መሎጊያዎቹ በቀለበቶቹ ውስጥ ይግቡ። [8]መሠዊያውን ውስጡን ባዶ ከሆኑ ሳንቃዎች አብጀው፤ ልክ በተራራው ላይ ባየኸው መሠረት ይበጅ።

## የመገናኛው ድንኳን አደባባይ

27፥9-19 ተጓ ምብ - ዘፀ 38፥9-20

[9]"ለመገናኛው ድንኳን አደባባይ አብጅለት፤ በደቡብ በኩል ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ[ሐ] ይሁን፣ ከቀጭን በፍታ የተፈተሉ መጋረጃዎች፣ [10]ሃያ ምሰሶዎች፣ ሃያ የነሐስ መቆሚያዎች፣ የብር ኰላቦችና በምሰሶቹም ላይ ዘንጎች ይኑሩት። [11]በሰሜኑም በኩል አንድ መቶ ክንድ ርዝመት ያላቸው መጋረጃዎች ይሁኑ፤ ሃያ ምሰሶዎቹ፣ ሃያ የነሐስ መቆሚያዎች፣ የብር ኰላቦችና በምሰሶዎችም ላይ ዘንጎች ይኑሩ።

[12]"የአደባባዩ ምዕራብ ጫፍ ስፋቱ አምሳ ክንድ[መ] ሆኖ ዐሥር ምሰሶዎችና ዐሥር መቆሚያዎች ያሉት መጋረጃዎች ይኑሩት። [13]በምሥራቅ ጫፍ በፀሐይ መውጫ በኩል ያለው አደባባይ አሁንም አምስት ክንድ ስፋት ይኑረው። [14]ሦስት ምሰሶዎችና ሦስት መቆሚያዎች ያሏቸው ርዝመታቸው ዐሥራ አምስት ክንድ[ሠ] የሆነ መጋረጃዎች በአንድ በኩል ባለው ደጃፍ ይሁኑ። [15]ሦስት ምሰሶዎች ሦስት መቆሚያዎች ያሏቸው ርዝመታቸው ዐሥራ አምስት ክንድ የሆነ መጋረጃዎች በሌላው በኩል ይሁኑ።

[16]"ለአደባባዩ መግቢያ አራት ምሰሶዎችና አራት መቆሚያዎች ያሉት ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና ከቀጭን በፍታ የተፈተለ፣ ጥልፍ ጠላፊ የጠለፈበት ሃያ ክንድ ርዝመት[ረ] ያለው መጋረጃ ይሁን። [17]በአደባባዩ ዙሪያ ያሉት ምሰሶዎች ሁሉ የብር ዘንጎች፣ ኰላቦችና የነሐስ መቆሚያዎች ይኑሯቸው። [18]አደባባዩ ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ፣ ስፋቱ አምሳ ክንድ[ሰ] ሆኖ፣ በቀጭኑ ከተፈተለ ማግ ቁመታቸው አምስት ክንድ[ሸ] የሆነ መጋረጃዎችና የነሐስም መቆሚያዎች ያሉት ይሁን። [19]ጥቅማቸው ምንም ዓይነት ይሁን፣ ለመገናኛው ድንኳን አገልግሎት የሚውሉ ዕቃዎች በሙሉ የድንኳኑና የአደባባዩ ካስማዎችም ሁሉ ሳይቀሩ ከነሐስ የተሠሩ ይሁኑ።

## የመቅረዙ ዘይት

27፥20-21 ተጓ ምብ - ዘሌ 24፥1-3

[20]"መብራቶቹ ባለማቋረጥ እንዲበሩ ለመብራቱ የሚሆን ተወቅጦ የተጠለለ ንጹሕ ዘይት እንዲያመጡልህ እስራኤላውያንን እዘዛቸው። [21]በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከመጋረጃው በስተ ውጭ ይኸውም ከምስክሩ ታቦት ፊት ለፊት፣ አሮንና ወንድ ልጆቹ

27፥1 ዘፀ20፥24፤ 40፥6፤1ነገ8፥64
27፥2 ዘፀ29፥12፤ 30፥2፤37፥25፤ ዘሌ4፥7፤1ነገ1፥50፤ 2፥28፤መዝ118፥27፤ ኤር17፥1፤ሕዝ43፥15 ፤አሞ3፥14፤ዘካ9፥15
27፥3 ዘኍ4፥14፤ 7፥13፤1ነገ7፥40:45፤ 2ነገ12፥13፤1ዜና 28፥17፤ኤር52፥18
27፥6 ዘፀ25፥13
27፥7 ዘፀ25፥14:28
27፥8 ዘፀ25፥9
27፥9 ዘፀ35፥17፤ 40፥8:33፤ዘሌ6፥16: 26፤ሕዝ40፥14፤ 42፥1
27፥16 ዘፀ40፥33፤ 36፥37
27፥20 ዘፀ25፥6
27፥21 ዘፀ16፥34፤ 25፥37፤28፥43፤ 29፥9:42፤30፥21: 36፤33፥7፤ዘሌ1፥1፤ 3፥17፤6፥26፤8፥3: 31፤16፥34፤17፥7፤ ዘኍ1፥1፤18፥23፤ 19፥21፤ 31፥54፤ ኢሱ18፥1፤1ነገ1፥39፤ 1ሳሙ30፥25

[ሀ]1 ወደ 1.3 ሜትር ያህል ነው።
[ለ]1 ርዝመቱ ወርዱ 2.3 ሜትር ያህል ነው
[ሐ]9 በዚህና በቍጥር 11 ላይ ወደ 46 ሜትር ያህል ነው።
[መ]12 በዚህና በቍጥር 13 ላይ ወደ 23 ሜትር ያህል ነው።
[ሠ]14 በዚህና በቍጥር 15 ላይ ወደ 6.9 ሜትር ያህል ነው።
[ረ]16 ወደ 9 ሜትር ያህል ነው።
[ሰ]18 ርዝመቱ 46 ሜትር፣ ወርዱ 23 ሜትር ያህል ነው።
[ሸ]18 ወደ 2.3 ሜትር ያህል ነው።

27፥1 *መሠዊያ፤* የሚቃጠል መሥዋዕት የሚሠዋበት ነው፤ (ዘሌ 4፥7:10:18 ይመ)፤ *ግራር እንጨት፤* የ25፥5 ማብ ይመ።

27፥2 *ቀንድ፤* በአራቱ ማዕዘን ምሰሶዎች ላይ የሚገኙ ጉጦች ናቸው፤ ቀንድ የእርዳታና የመማጠኛ ምልክት ሲሆን፣ (1ነገ 1፥50፡2፥28፤ መዝ 18፥2 ይመ)፣ መሠዊያው ያለውን የማስተሰረይ ኀይል ያሳያል። ደሙ በመሠዊያው እግሮች ሥር ከመረጨቱ በፊት በቀንዶቹ ላይ ይረጫል፤ (29፥12፤ ዘሌ 4፥7:18:25:30:34፡8፥15፡9፥9፡16፥18 ይመ)።

27፥3 *የዐመድ ማስወገጃ ምንቸቶችን፤* ከዐመድ ማውረጃው ላይ ዐመዱን ለማፍሰስ የሚረዱ ዕቃዎች ናቸው (ቍ 4 ይመ)፤ *መጫሪያዎችን፤* ዐመዱን ለመጥረግ የሚያገለግሉ ናቸው። *ጐድጓዳ ሳህኖች፤* የሚታረደውን እንስሳ ደም ለመያዝና በመሠዊያው እግሮች ላይ ለመርጨት የሚያገለግሉ ዕቃዎች ናቸው። *ሜንጦዎች፤* ሦስት ጣት ያላቸው ሹካዎች ሲሆኑ፣ የሚሠዋውን ሥጋ ለማስተካከል ወይም ሥጋው ከሚቀቀልበት አፍላል ውስጥ ለካህኑ የሚደርሰውን ሥጋ ለመለየት የሚረዱ ዕቃዎች ናቸው (1ሳሙ 2፥13-14 ይመ)። *የፍም መያዣዎች፤* ምናልባት የሚቃጠል መሥዋዕት ከሚሠዋበት መሠዊያ ላይ የእሳት ፍም ወስዶ በቅድስት ውስጥ በሚገኘው የዕጣን መሠዊያ ላይ ለመጨመር የሚያገለግሉ ሊሆኑ ይችላል (ዘሌ 10፥1:16፥12-13 ይመ)።

27፥4 *ዐመድ ማውረጃ፤* ሣጥን - መሰል ቅርጽ ባለው ዕቃ ላይ ከላይና ከታች ባለው ክፍል መካከል ላይ የሚገኝ ነው። በመሠዊያው አጋማሽ/እኩሌታ ላይ የሚነደው እሳት በርትቶ፣ የኋላ ኋላ መሠዊያውን ሊያወድመው ስለሚችል መሠዊያው አገልግሎት በሚሰጥበት ጊዜ በዐመድ መሙላት እንዲቻል ውስጡ ክፍት ሆኖ የተሠዋ ነው፤ (ቍ8 ይመ)። *ቀለበት፤* የ25፥12 ማብ ይመ።

27፥12-13 *ምዕራብ ጫፍ ... ምስራቅ ጫፍ፤* የማደሪያው አደባባይ እኩል ስፋት ያላቸው ሁለት ክፍሎች እንዳሉት ተገልጾአል። ቅድስተ ቅዱሳኑ በምዕራባዊው ክፍል መካከል ላይ ሲገኝ የሚቃጠል መሥዋዕት የሚቀርብበት መሠዊያ ደግሞ በምሥራቃዊው ክፍል መካከል ላይ ይገኛል።

27፥13-14 *በፀሐይ መውጫ በኩል ... ደጃፍ፤* ሰሎሞን ያሠራው ቤተ መቅደስና (ሕዝ 8፥16 ይመ) ሄሮድስ ያሠራው ቤተ መቅደስ መግቢያ በራቸው በምስራቅ በኩል እንደሆነ ሁሉ የማደሪያውም መግቢያ በር እንዲሁ በምስራቅ በኩል ነው።

27፥18 *አምስት ክንድ፤* ከአደባባዩ ውጭ የቆሙትን ሰዎች ዕይታ ለመጋረድ የሚችል ርዝመት ሲሆን፣ ይህም በአደባባዩ ውስጥ የሚፈጸመውን የአምልኮ ሥርዓት ቅድስና የሚጠብቅ ነው።

27፥20 *ንጹሕ ዘይት፤* ያልበሰሉ የወይራ ፍሬዎች በሙቀጫ ይወቀጣሉ። የወይራ ፍሬዎቹ ከተወቀጡ በኋላ ውቃጩ በጨርቅ ታስሮ ዘይቱ ቀስ እያለ እንዲንጠባጠብ ይጨመቃል፤ በዚህ ዐይነት የሚዘጋጀው ዘይት ንጹሕ በመሆኑ ሲነድ ጥቂት ጢስ ብቻ ሊኖረው ወይም ምንም ጢስ ላይኖረው ይችላል።

27፥21 *በመገናኛው ድንኳን፤* ማደሪያው ማለት ነው። ይህ ቦታ ሕዝቡ እግዚአብሔርን በኅብረት ለማምለክ የሚሰበሰብበት

መብራቶቹ ከምሽት እስከ ንጋት *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) *ፊት* እንዲበሩ ያድርጉ፤ ይህም በእስራኤላውያን ዘንድ ከትውልድ እስከ ትውልድ የዘላለም ሥርዐት ይሆናል።

## ልብሰ ተክህኖ

28 "ካህናት ሆነው ያገለግሉኝ ዘንድ ከእስራኤላውያን መካከል ወንድምህ አሮንን ከወንዶች ልጆቹ ከናዳብ፣ ከአብዩድ፣ ከአልዓዛርና ከኢታምር ጋር ወደ አንተ አቅርባቸው። [2]ለእርሱም ማዕረግና ክብር ለመስጠት ለወንድምህ ለአሮን የተቀደሱ መጐናጸፊያዎችን አብጅለት። [3]ካህን ሆኖ እንዲያገለግለኝ የተለየ ይሆን ዘንድ ጥበብ ለሰጠኋቸው በዚህ ጉዳይ ላይ ጥበበኛ ለሆኑ ሰዎች ሁሉ ለአሮን መጐናጸፊያዎችን እንዲሠሩለት ንገራቸው። [4]የሚሠሯቸው መጐናጸፊያዎች የደረት ልብስ ኤፉድ ቀሚስ፣ ጥልፍ ሸሚዝ፣ ጥምጥምና መታጠቂያ ናቸው፤ ካህን ሆነው ያገለግሉኝ ዘንድ የተቀደሱ መጐናጸፊያዎችን ለአሮንና ለወንድ ልጆቹ ይሠራሉ። [5]ወርቅ፣ ሰማያዊ፣ ሐምራዊ፣ ቀይ ማግና እንዲሁም ቀጭን በፍታ ይጠቀሙ።

## ኤፉድ

28፥6-14 ተጓ ምብ - ዘፀ 39፥2-7

[6]"የጥልፍ ዐዋቂዎች ኤፉዱን ከወርቅ፣ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ ይሥሩት። [7]መተሳሰር እንዲችል ሆኖ፣ ዳርና ዳር ከሚገኙት ከሁለቱ ጐኖች ጋር የተያያዙ ሁለት የትከሻ ንጣዮች ይኑሩት። [8]በጥበብ የተጠለፈው የወገብ መታጠቂያ ከወርቅ፣ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ ከኤፉድ ጋር አንድ ወጥ ሆኖ የተሠራ ይሁን።

[9]"ሁለት የመረግድ ድንጋዮች ውሰድና የእስራኤልን ልጆች ስሞቻቸውን ቅረጽባቸው። [10]እንደ ልደታቸው ቅደም ተከተል ስድስቱን ስሞች በአንዱ ድንጋይ ላይ የቀሩትንም ስሞች በሌላው ላይ ቅረጽባቸው። [11]የቅርጽ ሠራተኛ ማኅተም እንደሚቀርጽ የእስራኤልን ልጆች ስም በሁለቱ ድንጋዮች ላይ ቅረጽ፤ ከዚያም ድንጋዮቹን በወርቅ ፈርጥ ክፈፋቸው፤ [12]ለእስራኤል ልጆች መታሰቢያ ድንጋዮች ይሆኑ ዘንድ በኤፉዱ ትከሻ ላይ ካሉት ንጣዮች ጋር አያይዛቸው፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) *ፊት* መታሰቢያ እንዲሆኑ አሮን ስሞቹን በትከሻው ላይ ይሸከማቸው። [13]የወርቅ ፈርጦችን አብጅ፣ [14]እንደ ገመድ ያሉ ሁለት በንጹሕ ወርቅ የተጐነጐኑ ድሪዎችን አብጅተህ ከፈርጡ ጋር አያይዛቸው።

## የደረት ኪስ

28፥15-28 ተጓ ምብ - ዘፀ 39፥8-21

[15]"የፍርድ መስጫውን የደረት ኪስ ብልኀ ሠራተኛ እንደሚሠራው አድርገህ አብጀው፤ ልክ እንደ ኤፉዱ ከወርቅ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ አብጀው። [16]ርዝመቱ አንድ ስንዝር፣ ስፋቱ አንድ ስንዝር[a] ሆኖ ባለ አራት ማእዘንና በድርቡ የታጠፈ ይሁን። [17]ከዚያም በላዩ ላይ በአራት ረድፍ የከበሩ ድንጋዮች አድርግበት፤ በመጀመሪያው ረድፍ ሰርዲዮን፣ ቶጳዝዮን፣ የሚያብረቀርቅ ዕንቁ፤ [18]በሁለተኛውም ረድፍ በሉር፣ ሰንፔር[+]፣ አልማዝ፤ [19]በሦስተኛው ረድፍ ያክንት፣ ኬልቄዶን፣ አሜቴስጢኖስ፤ [20]በአራተኛውም ረድፍ ቢረሌ፣ መረግድና ኢያስጲድ[‡] አድርግበት፤ በወርቅ ፈርጥም ክፈፋቸው። [21]የዐሥራ ሁለቱ ነገዶች ስሞች እንደ ማኅተም የተቀረጸባቸው ለእያንዳንዱ የእስራኤል ልጆች ስም ዐሥራ ሁለት ድንጋዮች ይሁኑ።

[22]"ለደረት ኪሱ ከንጹሕ ወርቅ እንደ ገመድ ሆኖ የተጌጠ ጕንጕን አብጅለት።

[23]ለእርሱም ሁለት የወርቅ ቀለበቶች አብጅተህ ከደረት ኪሱ ሁለት ጎኖች ጋር አያይዘው። [24]ሁለቱን የወርቅ ጕንጕኖች በደረት ኪሱ ጐኖች ላይ ካሉት ቀለበቶች ጋር አያይዛቸው። [25]ሌሎቹን የጕንጕን ጫፎች በፊት ላይ ካለው ኤፉድ በትከሻው ላይ ካሉት ንጣዮች ጋር በማጋጠም ከሁለቱ የወርቅ ፈርጦች ጋር አያይዛቸው። [26]ሁለት የወርቅ ቀለበቶች አበጅተህ ከኤፉዱ ቀጥሎ ባለው በውስጠኛ ጠርዝ ላይ፣ በሌላ በኩል ካሉት ሁለት የደረት ኪስ ጕኖች ጋር አያይዛቸው። [27]ሁለት ተጨማሪ የወርቅ ቀለበቶች አበጅተህ ከኤፉዱ መታጠቂያ ከፍ ብሎ ከመጋጠሚያው አጠገብ ካለው በኤፉዱ ፊት ለፊት፣ በትከሻ ላይ ካሉት ንጣዮች

28፥1 ዘፀ6፥23፤ 24፥9፤ዘሌ8፥2፡30፤ 21፥1፤ዘኍ18፥1-7፤ ዘዳ18፥5፤1ሳሙ2፥28፤መዝ99፥6፤ ዕብ5፥1፡4
28፥2 ቍ40፤ ዘፀ29፥5፡29፤31፥10፤ 35፥19፤39፥11 ዘሌ8፥7-9፡30፤ 16፥32፤ ዘኍ20፥26-28
28፥3 ዘፀ31፥3፡6፤35፥10፡25፡35፤ 36፥1፤ዘዳ34፥9፤ ኢሳ11፥2፤1ቆሮ12፥8 ኤፌ1፥17
28፥4 ቍ15-30፡31-35፡37፡39፤ ዘፀ25፥7፤ዘሌ10፥5
28፥5 ዘፀ25፥4
28፥6 ዘፀ25፥7
28፥8 ዘፀ29፥5
28፥9 መኃ8፥6፤ ኢሳ49፥16፤ሐጌ2፥23
28፥12 ቍ29፤ ዘፀ30፥16፤ዘኍ10፥10፤ 31፥54፤ዘዳ33፥12፤ ኢዮ31፥36፤ ኢሱ4፥7፤ዘካ6፥14
28፥15 ዘፀ25፥7
28፥17 ሕዝ28፥13፤ ራእ21፥19-20
28፥20 ሕዝ1፥16፤ 10፥9፤ዳን10፥6
28፥21 ኢሱ4፥8፤ ራእ21፥12

[a]16 ወደ 22 ሴንቲ ሜትር ያህል ነው።
[+]18 ወይም፣ *ላፒስ ላዙሊ* ተብሎ መተርጐም ይቻላል።
[‡]20 የእነዚህ የከበሩ ማዕድኖች ትክክለኛ ማንነት በትክክል አይታወቅም።

ቦታ ሳይሆን፣ እግዚአብሔር ራሱ በቀጥሮ ከሕዝቡ ጋር የሚገናኝበት ቦታ ነው፤ (29፥42-43 ይመ)። *ከመጋረጃው ... ከምስክሩ ታቦት ፊት ለፊት፤* የ26፥31 ማብ ይመ። *መብራቶቹን ... ከምሽት እስከንጋት ... እንዲበሩ ያድርጉ፤* መብራቶቹ በምሽት ሲበሩ፤ (30፥8 ይመ) በንጋት ደግሞ ይጠፋሉ (1ሳሙ 3፥3)።

28፥1 *ከናዳብ፣ ከአብዩድ፤* የ24፥1 ማብ ይመ። *ካህናት ሆነው ያገለግሉኝ ዘንድ፤* ካህናት ሆነው የሚያገለግሉት፣ "ለኀጢአት ስርየት መሥዋዕትንና መባን እንዲያቀርቡ" እና "ምንም ሳያውቁ በተሳሳተ መንገድ የሚሄዱትን ለመመለስ" ነው፤ (ዕብ 5፥1-2)። ሌላው፣ የካህናት ትልቁ ሥራ የሙሴን ሕግ ለሕዝቡ ማንበብና በገቡት ቃል ኪዳን መሠረት እንዲኖሩ ማሳሰብ ነው፤ (ዘዳ 31፥9-13፤ ነህ 8፥2-3 ይመ)።

28፥2 *ማዕረግና ክብር፤* የክህነት ልብሱ የካህናቱንና (ቍ 40 ይመ)፣ የሊቀ ካህናቱን አገልግሎት ከፍ የሚያደርግ ነው።

28፥6 *ኤፉዱን፤* እጅጌ የሌለውና በሊቀ ካህናቱ የሚለበስ ልብሰ ተክህኖ ሲሆን፣ ቃሉ አንዳንድ ጊዜ በውል የማይታወቅ የማምለኪያን ዕቃ ያመለክታል፤ (ለምሳሌ መሳ 8፥27፡18፡17፤ ሆሴ 3፥4 ይመ)።

28፥8 *የወገብ መታጠቂያ፤* ኤፉድ ከካህናቱ አካል ጋር ከፊት ለፊትና ከጀርባው ያለውን ኤፉድን ከሊቀ ካህኑ አካል ከፊትና ከኋላ እንዲያያዝ/እንዲጣበቅ ለማድረግ ያገለግላል።

28፥12 *አሮን ... ስሞቹን በትከሻው ይሸከማቸው፤* ሊቀ ካህናቱ በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ሲያገለግሉ እስራኤላውያንን በሙሉ እንደሚወክሉ የሚያመለክት ነው።

28፥15 *ፍርድ መስጫውን፤* በኡሪምና በቱሚም አማካይነት ለማለት ነው፤ (የቍ 30 ማብ ይመ)።

ግርጌ ጋር አያይዘው። [28]የደረት ኪሱም ቀለበቶች፣ የደረት ኪሱ ከኤፉዱ ጋር እንዳይላቀቅ፣ ከመታጠቂያው ጋር በማገናኘት በሰማያዊ ገመድ ከኤፉዱ ቀለበቶች ጋር ይያያዙ።

[29]"አሮን ወደ መቅደሱ በሚገባበት ጊዜ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ለዘላለም መታሰቢያ ይሆን ዘንድ የእስራኤልን ልጆች ስሞች በፍርድ መስጫው ደረት ኪስ በልቡ ላይ ይሸከም። [30]ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት በሚገባበት ጊዜ በአሮን ልብ ላይ ይሆኑ ዘንድ ኡሪሙንና ቱሚሙን በደረት ኪሱ አድርግ፤ ስለዚህ አሮን ሁልጊዜ ለእስራኤላውያን የፍርድ መስጫውን *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት በልቡ ላይ ይሸከማል።

## ሌሎቹ አልባሳት

28፥31-43 ተጓ ምብ - ዘፀ 39፥22-31

[31]"የኤፉዱ ቀሚስ ሙሉ በሙሉ ከሰማያዊ ጨርቅ ይሁን፤ [32]ከላይ በኩል በመካከሉ ዐንገትጌ አድርገህ አብጀው፤ እንዳይቀደድም በማስገቢያው ዙሪያ እንደ ክሳድ ያለ ዝምዝም ጠርዝ[1] ሥራለት። [33]በጨርቁ ጠርዝ ዙሪያ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ ሮማኖቹን፣ በመካከሉም የወርቅ ሻኵራዎችን አብጅ። [34]የወርቅ ሻኵራዎቹና ሮማኖቹ በጨርቁ ጠርዝ ዙሪያ በመፈራረቅ ይሆናሉ። [35]አሮንም በአገልግሎቱ ጊዜ ይህን መልበስ አለበት፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ወደ መቅደሱ በገባና ከመቅደሱ ሲወጣ እንዳይሞት የሻኵራዎቹ ድምፅ ይሰማል።

[36]"ከንጹሕ ወርቅ ዝርግ ሳሕን አብጅተህ፣ "ቅዱስ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ)" በማለት በማኅተም ላይ እንደሚቀርጽ ቅረጸው። [37]ከመጠምጠሚያው ጋር እንዲያያዝ ሰማያዊ ፈትል እሰርበት፤ እርሱም በመጠምጠሚያው ፊት በኩል ይሁን። [38]ይህም በአሮን ግንባር ላይ ይሆናል፤ እስራኤላውያን ለይተው በሚያቀርቧቸው በማናቸውም የተቀደሱ ስጦታዎች ውስጥ ያለውን በደል ይሸከማል፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ተቀባይነት እንዲኖራቸው ሁልጊዜ በአሮን ግንባር ላይ ይሆናል።

[39]"ሸሚዙን ከቀጭን በፍታ ሥራ፤ መጠምጠሚያውንም ከቀጭን በፍታ አብጀው፤ መታጠቂያውንም ጥልፍ ጠላፊ የሠራው ይሁን። [40]የአሮን ወንድ ልጆች ክብርና ማዕረግ እንዲኖራቸው ሸሚዞችን፣ መታጠቂያዎችን፣ የራስ ማሰሪያዎችን አብጅላቸው። [41]እነዚህን ልብሶች ለአሮንና ለወንድ ልጆቹ ካለበስህ በኋላ ቅባቸው፤ ካናቸው፤ ካህናት ሆነው ያገለግሉኝም ዘንድ ቀድሳቸው።

[42]"ከወገብ ጀምሮ እስከ ጭን የሚደርስ ሰውነትን የሚሸፍን ከበፍታ የተሠራ የውስጥ ቁምጣ አብጅ። [43]አሮንና ወንድ ልጆቹ ወደ መገናኛው ድንኳን በሚገቡበት ጊዜ ወይም በመቅደሱ ለማገልገል ወደ መሠዊያው ሲቀርቡ፣ በደል ፈጽመው እንዳይሞቱ እነዚህን መልበስ አለባቸው።

"ለአሮንና ለትውልዶቹ ይህ የዘላለም ሥርዐት ይሆናል።

## የካህናት መቀደስ

29፥1-37 ተጓ ምብ - ዘሌ 8፥1-36

**29** "ካህናት ሆነው እንዲያገለግሉኝ ትቀድሳቸው ዘንድ የምታደርገው ይህ ነው፤ ነውር የሌለባቸው አንድ ወይፈንና ሁለት አውራ በጎች ውሰድ፤ [2]እርሾ ከሌለው ከምርጥ የስንዴ ዱቄት ቂጣ፣ በዘይት የተለወሰ የቂጣ እንጎቻና በዘይት የተቀባ ኅብስት ጋግር። [3]በሌማት ላይ አድርገህ ከወይፈኑና ከሁለቱ አውራ በጎች ጋር አቅርባቸው። [4]ከዚያም አሮንና ወንድ ልጆቹን ወደ መገናኛው ድንኳን ደጃፍ በማምጣት በውሃ እጠባቸው። [5]ልብሶቹን ወስደህ ለአሮን አልብሰው፤ ሸሚዝ፣ የኤፉድ ቀሚስ፣ ኤፉዱንና የደረት ኪሱን አልብሰው፤ ኤፉዱን በእርሱ ላይ በጥበብ በተሠራ መታጠቂያ እሠረው። [6]መጠምጠሚያውን በራሱ ላይ በማድረግ የተቀደሰውን አክሊል ከመጠምጠሚያው ጋር አያይዘው። [7]ቅብዐ ዘይት ወስደህ በራሱ ላይ በማፍሰስ ቅባው። [8]ወንዶች ልጆቹን አምጥተህ ሸሚዞች አልብሳቸው። [9]የራስ ማሰሪያዎችንም አድርግላቸው[2]፤ ከዚያም አሮንንና ወንዶች ልጆቹን መታጠ

28፥29 ቍ43
28፥30 ዘሌ8፥8፤ ዘኍ27፥21፤ ዘዳ33፥8፤ 1ሳሙ28፥6፤ ዕዝ2፥63፤ ነህ7፥65
28፥33 ዘኍ13፥23፤ 1ሳሙ14፥2፤ 1ነገ7፥18፤ ማሕ4፥3፤ ኤር52፥22፤ ኢል1፥12፤ ሐጌ2፥19
28፥36 ቍ37፤ ዘፀ29፥6፤ ዘሌ8፥9፤ ዘካ14፥20
28፥38 ዘፍ32፥20፤ ዘሌ5፥1፤10፥17፤ 16፥22፤22፥9፡16፡20፡ 27፤23፥11፤ ዘኍ18፥1፤ ኢሳ53፥5፡6፡11፤ ኢሳ56፥7፤ ሕዝ4፥4-6፤ ዕብ9፥28፤ 1ጴጥ2፥24
28፥39 ቍ4፤ ዘፀ29፥6፤ ዘሌ16፥4፤ ሕዝ24፥17፡23፤ 44፥18
28፥40 ቍ2፡4፤ ዘፀ29፥8-9፤39፥41፤ 40፥14፤ ዘሌ8፥13
28፥41 ዘፀ29፥7-9፤ 30፥30፤40፥13፡15፤ ዘሌ4፥3፤6፥20፡22፤ 8፥1-36፤10፥7፤ 21፥12፤ ዘኍ3፥3፤ 35፥25፤ ዕብ7፥28
28፥42 ዘሌ6፥10፤ 16፥4፡23፤ ሕዝ44፥18
28፥43 ቍ29፤ ዘፀ27፥21፤30፥20፡ 21፤27፥21፤ ዘሌ16፥13፤22፥9፤ ዘኍ1፥51፤ 4፥15፡20፤18፥22
29፥1 ቍ21፡44፤ ዘሌ20፥7፤ ኢሱ3፥5፤ 1ዜና15፥12፤ ሕዝ43፥23
29፥2 ቍ23፤ ዘሌ2፥1፡4፤6፥19-23፤ ዘኍ6፥15
29፥3 ቍ15፡19
29፥4 ዘፀ40፥12፤ ዘሌ14፥8፤16፥4፤ ዕብ10፥22
29፥5 ዘፀ28፥2፡8
29፥6 ዘፀ28፥36፡ 39፤ ኢሳ3፥23፤ ዘካ3፥5
29፥7 ቍ21፤ ዘፀ28፥41፤30፥25፡ 30፡31፤37፥29፤ 40፥9፤ ዘሌ21፥10፤ 1ሳሙ10፥1፤ 1ነገ1፥39፤ መዝ89፥20፤ 133፥2፤141፥5
29፥8 ዘፀ28፥4፤ ዘሌ16፥4
29፥9 ዘፀ28፥40፤ 27፥21፤40፥15፤ ዘኍ3፥10፤18፥7፤25፥13፤ ዘዳ18፥5፤ መሳ17፥5፤ 1ሳሙ2፥30፤ 1ነገ12፥31

[1] 32 በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትክክለኛ ፍቺው አይታወቅም።
[2] 9 ዕብራይስጡ፣ *የሰላም መሥዋዕት አድርግላቸው* ይላል።

28፥29 *አሮን ... የእስራኤልን ልጆች ስሞች ... በልቡ፤* በዚህ ዐይነት ሕዝበ እስራኤል በሙሉ በእግዚአብሔር ፊት ይወከላል (ቍ 12 እና ማብ ይመ)።

28፥30 *ኡሪሙንና ቱሚሙን፤* ይህን ሐረግ ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል "ርግማንና ፍጹማን" የሚል ትርጕም ሳይኖረው አይቀርም። ኡሪም የሚለው የዕብራይስጡ ቃል፣ "አሌፍ" በሚለው የዕብራይስጡ የመጀመሪያ ሆሄ ሲጀምር፣ ቱሚም የሚለው "ታው" በሚለው የመጨረሻው ሆሄ ይጀመራል። ኡሪምና ቱሚም እንደ ቅዱስ ዕጣ ወይም ዕድል ፈንታ የሚታዩና በመከራ ጊዜ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለማወቅ የሚያገለግሉ ናቸው፤ (ዘኍ 27፥21 ይመ)። ዕጣው ሲጣል ከዕጣው ውስጥ አብዛኛው እጅ ኡሪም ("ርግማን") ከሆነ መልሱ "አይደለም" ይሆናል፤ ነገር ግን ቱሚም ("ፍጹማን") ከወጣ መልሱ "አዎን" ይሆናል። ያም ሆነ ይህ የዕጣውን ውሳኔ የሚሰጥ እግዚአብሔር ነው፤ (ምሳ 16፥33)።

28፥31 *የኤፉድ ቀሚስ፤* ከኤፉድ ሥር የሚለበስ ነው።

*28፥35፤* በአይሁዳውያን ልማድ መሠረት የገመዱ አንዱ ጫፍ ከሊቀ ካህናቱ ጉልበት ጋር የሚታሠር ሲሆን፣ የቀረው ጫፍ ደግሞ ከማደሪያው ውጭ እንዲሆን ይደረጋል። ሊቀ ካህናቱ በቅድስት እያለ በቀሚሱ ላይ የታሠሩት ቃጭሎች ማቃጨላቸውን ካቆሙ፣ ሞቷል ተብሎ ስለሚታሰብ ገመዱን ቀስ ብሎ በመጐተት ሁኔታው ይረጋገጣል።

28፥38 *በደል ... ይሸከማል፤* በምሳሌነት ማለት ነው።

28፥39 *ሸሚዝ፤* ከቀሚሱ በታች የሚለበስ ነው።

28፥40 *ክብርና ማዕረግ፤* የቍ 2 ማብ ይመ።

*28፥42-43፤* የ20፥26 ማብ ይመ።

28፥43 *መገናኛው ድንኳን፤* የ27፥21 ማብ ይመ።

29፥1 *ትቀድሳቸው፤* የ19፥10-11 ማብ ይመ። *ነውር የሌለባቸውን፤* የ12፥5 ማብ ይመ።

29፥4 *መገናኛው ድንኳን፤* የ27፥21 ማብ ይመ። *በውሃ እጠባቸው፤* በሥርዐቱ መንጻትን ያመለክታል፤ (ከዕብ10፥22 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይህም በሕይወታቸው ሊታይ የሚገባውን ንጽሕና ያሳያል።

29፥7 *ቅባው፤* እግዚአብሔርን ለማገልገል የሚሰጠውን

ቂያዎችን አስታጥቃቸው፤ ክህነት የዘላለም ሥርዐት ይሆንላቸዋል፤ በዚህም መንገድ አሮንንና ወንዶች ልጆቹን ትክናቸዋለህ።

[10]“ወይፈኑን በመገናኛው ድንኳን ፊት ለፊት በማምጣት አሮንና ወንዶች ልጆቹ በራሱ ላይ እጆቻቸውን ይጫኑበት። [11]በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ *በእግዚአብሔር* (ያሕዌ) ፊት እረደው። [12]ከወይፈኑ ደም ወስደህ በመሠዊያው ቀንዶች ላይ በጣቶችህ አድርግበት፤ የቀረውንም ከመሠዊያው ሥር አፍስሰው። [13]ከዚያም በሆድ ዕቃዎች ያለውን ስብ ሁሉ፣ የጉበቱን መሸፈኛና ሁለቱንም ኵላሊቶች በዙሪያቸው ካለው ስብ ጋር ወስደህ በመሠዊያው ላይ አቃጥላቸው። [14]ነገር ግን የወይፈኑን ሥጋ፣ ቆዳውንና የማይበላውን እሰስ ገሥስ ሥጋ ከሰፈር ውጭ አቃጥለው፤ የኀጢአት *መሥዋዕት* ነው።

[15]“ከሁለቱ አውራ በጎች አንዱን ወስደህ፣ አሮንና ወንዶች ልጆቹ በራሱ ላይ እጃቸውን ይጭኑበታል። [16]አውራውንም በግ እረደው፤ ደሙንም ወስደህ በመሠዊያው ላይ ዙሪያውን እርጨው። [17]አውራ በጉን በየብልቱ ቆራርጠህ፣ የሆድ ዕቃውንና እግሮቹን አጥበህ ከራሱና ከሌሎቹ ቁርጥራጭ ብልቶች ጋር አኑረው። [18]ከዚያም አውራ በጉን በሙሉ በመሠዊያው ላይ አቃጥለው፤ *ለእግዚአብሔር* (ያሕዌ) የሚቃጠል *መሥዋዕት* ጣፋጭ መዓዛና *ለእግዚአብሔር* (ያሕዌ) በእሳት የሚቀርብ *መሥዋዕት* ነው።

[19]“ሌላውን አውራ በግ ወስደህ አሮንና ወንዶች ልጆቹ በራሱ ላይ እጆቻቸውን ይጭኑበታል። [20]አውራውንም በግ እረደው፤ ከደሙም ወስደህ የአሮንንና የወንዶች ልጆቹን የቀኝ ጆሮዎቻቸውን ጫፍ የቀኝ እጆቻቸውን አውራ ጣቶች፣ የቀኝ እግራቸውንም አውራ ጣቶች ቅባቸው፤ ከዚያም ደሙን በመሠዊያው ላይ ዙሪያውን እርጨው። [21]በመሠዊያው ላይ ካለው ደምና ከቅብዐ ዘይቱ ወስደህ በአሮንና በልብሶቹ ላይ እንዲሁም በወንዶች ልጆቹና በልብሶቻቸው ላይ እርጨው። ከዚያም እርሱና ወንዶች ልጆቹ እንዲሁም ልብሶቻቸው የተቀደሱ ይሆናሉ።

[22]‘ከዚህ አውራ በግ ስቡን፣ ላቱን፣ በሆድ ዕቃው ውስጥ ያለውን ስብ፣ የጉበቱን ሽፋን፣ ሁለቱን ኵላሊቶችና በዙሪያቸው ያለውን ስብና ቀኙን ወርች ውሰድ፤ ይህ የክህነት አውራ በግ ነው። [23]*በእግዚአብሔር* (ያሕዌ) ፊት በሌማት ካለው ያለ እርሾ ከተጋገረው ቂጣ፣ ዳቦ፣ በዘይት የተሠራ እንጎቻና ኅብስት ውሰድ። [24]እነዚህን ሁሉ በአሮንና በወንዶች ልጆቹ እጆች ላይ በማኖር እንደሚወዘወዝ *መሥዋዕት በእግዚአብሔር* (ያሕዌ) ፊት ወዝውዛቸው። [25]ከዚያም ከእጆቻቸው ወስደህ ከሚቃጠለው *መሥዋዕት* ጋር *ለእግዚአብሔር* (ያሕዌ) መልካም መዓዛ እንዲሆን በመሠዊያው ላይ አቃጥለው፤ ይህም *ለእግዚአብሔር* (ያሕዌ) በእሳት የሚቃጠል *መሥዋዕት* ነው። [26]ለአሮን ክህነት የአውራ በጉን ፍርምባ ከወሰድህ በኋላ እንደሚወዘወዝ *መሥዋዕት በእግዚአብሔር* (ያሕዌ) ፊት ወዝውዘው ይህም የአንተ ድርሻ ይሆናል።

[27]“ለአሮንና ለወንዶች ልጆቹ ለክህነት የሆኑትን የአውራውን በግ ብልቶች፣ ቀድሳቸው። የተወዘወዘውን ፍርምባና የቀረበውን ወርች [28]ለአሮንና ለወንዶች ልጆቹ የዘወትር የእስራኤላውያን ድርሻ የሚሆነው ይህ ነው፤ ከኅብረት *መሥዋዕታቸው*[1] እስራኤላውያን *ለእግዚአብሔር* (ያሕዌ) የሚያቀርቡት ነው።

[29]“የአሮን የተቀደሱ ልብሶች ለትውልዶቹ ይሆናሉ፤ ይኸውም በእነርሱ ይቀቡና ክህነትን ይቀበሉ ዘንድ ነው። [30]ካህን በመሆን እርሱን የሚተካውና በመቅደሱ ለማገልገል ወደ መገናኛው ድንኳን የሚመጣው ወንድ ልጅ ሰባት ቀን ይለብሳቸዋል።

[31]“የክህነቱን አውራ በግ ወስደህ ሥጋውን በተቀደሰ ስፍራ ቀቅለው። [32]አሮንና ወንዶች ልጆቹ በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ የአውራውን በግ ሥጋና በሌማት ያለውን ዳቦ ይብሉ። [33]ለክህነታቸውና ለመቀደሳቸው ማስተስረያ የሆኑትን እነዚህን *መሥዋዕቶችን* ይብሉ፤ የተቀደሱ ስለ ሆኑ ሌላ ማንም አይብላቸው። [34]ከክህነቱ የአውራ በግ ሥጋ ወይም ከቂጣው እስከ ንጋት ድረስ ቢተርፍ አቃጥለው፤ የተቀደሰ ስለሆነ መበላት የለበትም።

[35]“ክህነታቸውን በሰባት ቀን በመፈጸም ለአሮንና ለወንዶች ልጆቹ ያዘዝሁህን ሁሉ አድርግላቸው። [36]ለማስተስረያ የሚሆን አንድ

[1]28 በትውፊት፣ *የሰላም መሥዋዕት* በመባል ይታወቃል

29፥10 ቍ19፤ ዘሌ1፥4፤4፥15፤ 16፥21፤ዘኍ8፥12
29፥11 ዘሌ1፥5፡ 11፤4፥24፤6፥16፡ 25፤14፥13
29፥12 ዘፀ27፥2፤ ዘሌ4፥7፤9፥9
29፥13 ቍ22፤ ዘፀ12፥9፤ዘሌ1፥8፤ 3፥3፡5፡9፤4፥10፤6፥ 12፤7፥3፡5፡31፤9፥10፤ ዘኍ18፥17፤1ሳሙ2፥ 15፤1ነገ8፥64፤ 2ዜና7፥7፤29፥35፤ 35፥14፤ኢሳ43፥24፤ ሕዝ 44፥15፤
29፥14 ዘሌ4፥12፡ 21፤16፥27፤ ዘኍ19፥3-5፤ናሆ3፥ 6፤ሚል2፥3፤ ዕብ13፥11
29፥15 ቍ3፡10፤ ዘሌ3፥2፤2ዜና29፥23
29፥17 ዘሌ1፥9፡13
29፥18 ዘፍ8፥21፤ 2ቆሮ2፥15
29፥19 ቍ3፡10
29፥20 ቍ16፤ ዘሌ1፥5፡11፤ 3፥2፤14፥14፡25
29፥21 ቍ1፡7፤ ዕብ9፥22
29፥22 ቍ13
29፥24 ዘሌ7፥30፤ 9፥21፤10፥15፤14፥ 12፤23፥11፡20፤ ዘኍ6፥20፤8፥11፡13፡ 15
29፥25 ቍ18
29፥26 ዘሌ7፥31፡ 34
29፥27 ዘፀ22፥29፤ ዘሌ7፥31፡34፤ ዘኍ18፥11፡12፤ ዘዳ18፥3
29፥28 ቍ22-27፤ ዘሌ7፥30፡34፤10፥15
29፥29 ዘፀ28፥2፤ ዘሌ16፥4፤ዘኍ20፥28
29፥30 ዘሌ6፥22፤ ዘኍ 3፥3፤20፥28
29፥31 ዘሌ7፥37፤ 10፥14፤ዘኍ19፥9፤ 2ዜና13፥9፤ ሕዝ42፥13
29፥32 ማቴ12፥4
29፥33 ዘሌ22፥10፡ 13
29፥34 ዘፀ12፥10
29፥36 ቍ33፡37፤ ዘፀ30፥10፤40፥10፤

*መንፈሳዊ ብቃት ያመለክታል፤* (ኢሳ 61፥1 ይመ)።

29፥10 *ወይፈኑን ... በማምጣት፤* የአሮንንና የልጆቹን የቀደመ ኀጢአት ለማስተሰረይ፣ (ዘሌ 4፥3 ይመ) እንደ ኀጢአት *መሥዋዕት* ሆኖ የሚቀርብ ነው፤ (ቍ14 ይመ) *በራሱ ላይ እጆቻቸውን ይጫኑበት፤* ይህ የሚያመለክተው (1) እንስሳው በእነርሱ ምትክ መሠዋቱንና (2) ኀጢአታቸው ኀጢአትን በሚሸከመው ላይ መተላለፉን ነው፤ (ዘሌ 16፥20-22 እና ማብ ይመ)።

29፥12 *በመሠዊያው ቀንዶች ላይ፤* የ27፥2 ማብ ይመ።

29፥13 *ስብ፤ የወይፈኑ ምርጥ ብልት ሁሉ፣* (ዘሌ3፥3-5፡16) *መሥዋዕት* ሆኖ በመቃጠል በእግዚአብሔር ፊት ይቀርባል።

29፥14 *ሥጋ ፤ ቆዳውንና የማይበላውን እሰስ ገሰስ፤* ኀጢአቱን የሚሸከም ነው ተብሎ ስለሚታሰብ፣ ከሠፈሩ ውጭ ይቃጠላል፤ (ዕብ 13፥11-13 ይመ)።

29፥18 *በጉን በሙሉ ... አቃጥለው፤* ፈጽሞ ከልብ መሰጠትን ያመለክታል።

29፥20 *ቀኝ ጆሮዎቻቸውን፤* ለእግዚአብሔርና ለቃሉ ንቁ መሆንን ያመለክታል። *ቀኝ እጆቻቸውን... ቀኝ እግሮቻቸውን፤* በእግዚአብሔር ምትክ ለሌሎች የሚሰጠውን አገልግሎት ያመለክታል።

29፥24 *እንደሚወዘወዝ መሥዋዕት፤* የዘፀ 7፥30-32 ማብ ይመ።

29፥28 *ለአሮንና ... ልጆቹ ... ድርሻ፤* ከሚሠውት እንስሳት የተወሰነው ክፍል ለካህናቱና ለቤተሰቦቻቸው ምግብ እንዲሆን ይመደብ ነበር፤ (ዘሌ 10፥14 ይመ)።

29፥31 *በተቀደሰ ስፍራ፤* ምናልባት የማደሪያውን አደባባይ ሳይሆን አይቀርም።

ወይፈን የኀጢአት መሥዋዕት አድርገህ በየዕለቱ ሠዋ፤ ለመሠዊያውም ማስተስረያ በማቅረብ መሠዊያውን አንጻው፤ ትቀድስ ውም ዘንድ ቅባው። [37]ለሰባት ቀን ለመሠ ዊያው ማስተስረያ በማድረግ ቀድሰው፤ ከዚ ያም መሠዊያው እጅግ የተቀደሰ ይሆ ናል፤ የሚነካውም ሁሉ የተቀደሰ ይሆናል።

[38]"በየዕለቱ ያለማቋረጥ በመሠዊያው ላይ የምታቀርበው ይህ ነው፤ ዓመት የሞ ላቸው ሁለት የበግ ጠቦቶች፤ [39]አንዱን በማ ለዳ፣ ሌላውን በምሽት አቅርብ። [40]ከመጀ መሪያው የበግ ጠቦት ጋር የኢፍ መስፈሪያ አንድ ዐሥረኛ[a] ምርጥ ዱቄትን ተወቅጦ ከተጠለለ ሩብ ኢፍ[b] ዘይት ጋር ለውስና ሩብ ኢን ወይንን ደግሞ የመጠጥ መሥዋዕት በማድረግ አቅርብ። [41]ሌላውን የበግ ጠቦት በማለዳው እንደ ቀረበው ተመሳሳይ ከሆነው የእህልና የመጠጥ መሥዋዕት ጋር በምሽት ሠዋው፤ ይህም ባፋጭ መዐዛና ለእግዚ አብሔር (ያህዌ) በእሳት የሚቀርብ መሥዋዕት ነው።

[42]"ይህ የሚቃጠል መሥዋዕት በእግዚ አብሔር (ያህዌ) ፊት በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ በሚመጡት ትውልዶች ዘወትር ይደረጋል፤ በዚያ እገናኝሃለሁ፤ እናገርሃለ ሁም፤ [43]በዚያ ደግሞ ከእስራኤላውያን ጋር እገናኛለሁ፤ ስፍራውም በክብሬ ይቀደሳል።

[44]"ስለዚህ የመገናኛው ድንኳንና መሠዊ ያውን እኔ እቀድሳለሁ፤ ካህናት ሆነው እንዲያገለግሉኝ አሮንና ወንድ ልጆቹን እቀድሳለሁ። [45]ከዚያም በእስራኤላውያን መካ ከል እኖራለሁ፤ አምላካቸውም (ኤሎሂም) እሆና ለሁ። [46]በመካከላቸውም እኖር ዘንድ ከግ ብፅ ያወጣኋቸው እኔ አምላካቸው እግዚአ ብሔር (ያህዌ) መሆኔን ያውቃሉ፤ እኔ እግዚ አብሔር (ያህዌ) አምላካቸው ነኝ።

## የዕጣን መሠዊያ

30፥1-5 ተጓ ምብ - ዘፀ 37፥25-28

**30** ዕጣን የሚጤስበት መሠዊያ ከግ ራር ዕንጨት ሥራ። [2]ርዝመቱና ጐኑ ባለ አንድ አንድ ክንድ[c] የሆነ ከፍታ ውም ሁለት ክንድ የሆነ አራት ማእዘን ይሁን፤ ከመሠዊያው ጋር አንድ ወጥ የሆኑ ቀንዶች ይኑሩት። [3]ላዩን፣ ጐኖቹን ሁሉና ቀንዶቹን በንጹሕ ወርቅ ለብጣቸው፤ ዙሪያ ውን የወርቅ ክፈፍ አብጅለት። [4]መሠዊያ ውን ለመሸከም የሚያገለግሉትን መሎጊያዎች የሚይዙ፣ ከክፈፉ በታች ትይዩ የሆኑ ሁለት የወርቅ ቀለበቶችን ለመሠዊያው አብጅ። [5]መሎጊያዎቹንም ከግራር እንጨት ሠርተህ በወርቅ ለብጣቸው። [6]መሠዊያውን ከመጋረጃው ፊት ለፊት፣ ይኸውም ከምስክሩ ታቦት ፊት፣ ከምስክሩ በላይ ካለው እኔ አንተን ከምገናኝበት ከስርየት መክደኛው ፊት አስ ቀምጠው።

[7]"አሮን መብራቶቹን በሚያዘጋጅበት ጊዜ፣ በየማለዳው ደስ የሚያሰኝ ሽታ ዕጣን በመሠዊያው ላይ ያጢስ። [8]ምሽት ላይ መብራቶቹን በሚያበራበትም ጊዜ ዕጣኑን ማጠን አለበት፤ ይኸውም በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ ዕጣኑ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ዘወትር እንዲጤስ ነው። [9]በዚህም መሠ ዊያ ላይ ሌላ ዕጣን ወይም ሌላ የሚቃጠል መሥዋዕት ወይም የእህል መሥዋዕት አታ ቅርብ፤ የመጠጥ መሥዋዕትም አታፍስበት። [10]አሮን በዓመት አንድ ጊዜ በቀንዶቹ ላይ ማስተስረያ ያደርግበታል፤ ይህ ዓመታዊ ማስተስረያ በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ ለማስተስረያ ከሚሆን የኀጢአት መስዋዕት ደም ጋር መደረግ አለበት፤ ይህም ለእግዚ አብሔር (ያህዌ) እጅግ ቅዱስ ነው።"

## የማስተስረያ ገንዘብ

[11]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ [12]"የእስራኤላውያንን ጠቅላላ ቈጠራ በምታደርግበት ጊዜ እያንዳንዱ ሰው በሚ ቈጠርበት ወቅት ለሕይወቱ ቤዛ የሚሆን ዎጆ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መክፈል አለበት፤ በዚህም ዐይነት ስትቈጥራቸው በእነርሱ ላይ መቅሠፍት አይመጣም። [13]ማንም ወደ ተቈጠሩት ዘንድ የሚያልፍ ሃያ አቦሊ በሚመዝን በመቅደሱ ሰቅል ሚዛን ግማሽ ሰቅል[d] መስጠት አለበት፤ ይህ ግማሽ ሰቅል

ዘሌ1፥4፤4፥20፤16፥16፤ዘኍ6፥11፤7፥10፤8፥12፡19፤16፥46፤25፥13፤2ዜና29፥24፤ዕብ10፥11
29፥37 ዘፀ30፥28-29፤40፥10፤ሕዝ43፥25፤ማቴ23፥19
29፥38 ዘሌ23፥2፤ዘኍ28፥3-8፤1ዜና16፥40፤2ዜና8፥13፤ሕዝ46፥13-15፤ዳን12፥11
29፥39 ዘኍ28፥4፡8፤1ነገ18፥36፤2ዜና13፥11፤ዕዝ3፥3፤መዝ141፥2፤ዳን9፥21
29፥40 ዘፍ35፥14፤ዘፀ30፥24፤ዘሌ23፥37፤ዘኍ15፥4፤28፥5፤2ነገ16፥13
29፥41 ዘሌ2፥1፤5፥13፤10፥12፤ዘኍ4፥16፤6፥17፤1ነገ18፥64፤18፥29፡36፤2ነገ3፥20፤16፥15፤ዕዝ9፥4፡5፤መዝ141፥2፤ኢሳ43፥23፤ዳን9፥21
29፥42 ቍ43፤ዘፀ25፥42፤26፥1፡22፤27፥21፤30፥8፡10፡21፡31፤31፥13፤33፥9፡11፤ዘኍ7፥89፤ሕዝ46፥15
29፥43 ዘፀ33፥18፤40፥34፤ዘሌ9፥6፤1ነገ8፥11፤2ዜና5፥14፤7፥2፤መዝ26፥8፤85፥9፤ሕዝ1፥28፤43፥5፤ሐጌ1፥8፤2፥7
29፥44 ቍ1
29፥45 ዘፍ17፥7፤ዘፀ25፥8፤ዘኍ35፥34፤ዮሐ14፥17፤ሮሜ8፥10፤2ቆሮ6፥16
29፥46 ዘፍ17፥7፤ዘፀ6፥6፤19፥4-6፤ዘዳ5፥6፤መዝ114፥1፤ሐጌ2፥5
30፥1 ዘፀ25፥6፤37፥29፤40፥5፡26፤ዘኍ4፥11፤1ነገ6፥20፤ሕዝ41፥22፤25፥6፤37፥29፤ሉቃ1፥11፤ዕብ9፥4፤ራእ8፥3
30፥2 ዘፀ27፥2፤ራእ9፥13
30፥3 ዘፀ25፥11
30፥4 ዘፀ25፥12
30፥5 ዘፀ25፥13
30፥6 ዘፀ25፥22፤26፥34
30፥7 ዘፀ25፥6፤40፥27፤ዘኍ3፥10፤ዘዳ33፥10፤1ሳሙ2፥28፤1ዜና6፥49፤2ዜና2፥4፤26፥18፤29፥7 30፥8 ዘፀ25፥37፤29፥42
30፥9 ዘሌ10፥1፤ዘኍ16፥7፡40 30፥10 ዘፀ29፥14፡42፤ዘሌ4፥3፤6፥25፤7፥7፤8፥2፡14፤9፥7፤16፥2፤ 16፥18-19፡30፤23፥27፡28፤25፥9፤ዘኍ6፥11 30፥12 ዘፀ38፥25፡ 26፤ዘኍ1፥2፡49፤4፥2፡29፤14፥29፡12፤ 26፥2፤31፥26፡50፤ ዘዳ 28፥58-61፤2ሳሙ24፥1፤24፥13፤1ነገ8፥37፤2ነገ12፥4፤ማቴ20፥28 30፥13 ቍ24፤ዘፀ38፥24፡26፤ ዘሌ5፥15፤27፥3፡25፤ ዘኍ3፥47፤7፥13፤ 18፥16፤ሕዝ4፥10፤ 45፥12፤ማቴ17፥24

[a] 40 ይህ ምናልባት 2 ሊትር ያህል ነው።
[b] 40 ይህ ምናልባት 1 ሊትር ያህል ነው።
[c] 2 ርዝመቱና ጐኑ 0.5 ሜትር፣ ከፍታው 0.9 ሜትር ያህል ነው።
[d] 13 በዚህና በቍጥር 15 ላይ 6 ግራም ያህል ነው።

*29፥38-39፤* በየዕለቱ ጠዋትና ማታ ሳይታጐል መቅረብ ስላለበት መሥዋዕት የተሰጠው ሥርዐት ሲሆን፣ ይህ ሥርዐት የእግዚአብሔር ሕዝብ መናፍቅ በነበረበት ዘመንም እንኳ ይደረግ ነበር (2ነገ 16፥15 ይመ)።

29፥42-43 *በዚያ እገናኝሃለሁ፤ እናገርሃለሁም፤* የ27፥21 ማብ ይመ።

29፥43 *በክብሬ፤* በኪዳኑ ታቦት ላይ የእግዚአብሔርን መገ ኘት ያመለክታል፤ (የ25፥1፡40፥34-35፤1ነገ8፥10-13 ማብ ይመ)።

*29፥45-46፤ መካከል እኖራለሁ፤* የ25፥9 ማብ ይመ።

29፥45 *አምላካቸውም እሆናለሁ፤* እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የገባውን ቃል ኪዳን ለማመልከት ነው፤ (የ6፥7 ማብ ይመ)።

29፥46 *ከግብፅ ያወጣኋቸው እኔ አምላካቸው እግዚአብሔር፤* የ20፥2 ማብ ይመ።

30፥1 *ዕጣን፤* የዕጣኑ ሽታ የእግዚአሔርን ሕዝብ ጸሎት ያመለክታል፤ (መዝ141፥2፤ ሉቃ1፥10፤ ራእ5፥8፡8፥3-4 ይመ)።

30፥3 *ወርቅ፤* የ26፥37 ማብ ይመ።

30፥4 *ቀለበቶችን፤* የ25፥12 ማብ ይመ።

30፥6 *ከመጋረጃው ፊት ለፊት ... ከምስክሩ ታቦት፤* የ25፥16፡22፡26፥31 ማብ ይመ።

30፥10 *ዓመታዊ ማስተስረያ፤* ዘሌ 16፥34 ይመ።

30፥12 *የእስራኤላውያንን ... በሚቈጠርበት፤* ምናልባት እንዲህ ያለው ቈጠራ የሚደረገው በተለያዩ ጊዜያት ሲሆን፣ የሚደረገውም እስራኤላውያን በእግዚአብሔር አገልግሎት ውስጥ ተሳትፎ እንዲኖራቸው ለማድረግ ነው፤ (ዘኍ 1፥2፡26፥2 ይመ)። *ለሕይወቱ ... ዎጆ ... መክፈል አለበት፤* በ13፥13፡15 ላይ

ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የሚቀርብ መሥዋዕት ነው:: [14]ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከሃያ በላይ ሆኖ ወደ ተቈጠሩት ያለፉት ሁሉ፣ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መሥዋዕት ማቅረብ አለባቸው:: [15]ለሕይወታችሁ ማስተስረያ እንዲሆን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መሥዋዕት በምታቀርቡበት ጊዜ ባለጠጋው ከግማሽ ሰቅል በላይ፣ ድኻውም አጕድሎ አይስጥ:: [16]የማስተሰረያውን ገንዘብ ከእስራኤላውያን ተቀብለህ ለመገናኛው ድንኳን አገልግሎት አውለው፤ ለሕይወታችሁ ማስተስረያ በማድረግ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት የእስራኤላውያን ማስተስረያ ይሆናል::"

## የመታጠቢያ ሰን

[17]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ [18]"ለመታጠቢያ ከናስ ማስቀመጫው ጋር የናስ ሰን አብጅ፤ በመገናኛው ድንኳንና በመሠዊያው መካከል አስቀምጠህ ውሃ አድርግበት:: [19]አሮንና ወንዶች ልጆቹ በውስጡ ባለው ውሃ እጃቸውንና እግራቸውን ይታጠቡበታል:: [20]ወደ መገናኛው ድንኳን በሚገቡበት ጊዜ ሁሉ እንዳይሞቱ በውሃ ይታጠቡ፤ እንዲሁም ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የእሳት መሥዋዕት ለማቅረብ ወደ መሠዊያው ለማገልገል በሚቀርቡበት ጊዜ፣ [21]እንዳይሞቱ እጃቸውንና እግራቸውን ይታጠባሉ፤ ይህም በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ ለአሮንና ለትውልዶቹ የዘላለም ሥርዐት ይሆናል::"

## ቅብዐ ዘይት

[22]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፣ [23]"ምርጥ ቅመሞችን፣ አምስት መቶ ሰቅል[a] ፈሳሽ ከርቤ፣ ግማሽ ይኸውም ሁለት መቶ አምሳ ሰቅል ጣፋጭ ቀረፋ፣ ሁለት መቶ አምሳ ሰቅል ጠጅ ሣር፣ [24]አምስት መቶ ሰቅል ብርጕድ ውሰድ፤ ሁሉም እንደ መቅደሱ ሰቅልና አንድ የኢን መስፈሪያ[b] የወይራ ዘይት ይሁን፤ [25]እነዚህን በቀማሚ እንደ ተሠራ እንደሚሸት ቅመም የተቀደሰ ቅብዐ ዘይት አድርግ፤ የተቀደሰ ቅብዐ ዘይት ይሆናል፤ [26]ከዚያም የመገናኛውን ድንኳን፣ የምስክሩን ታቦት፣ [27]ጠረጴዛውንና ዕቃዎቹን ሁሉ፣ መቅረዙንና ዕቃዎቹን፣ የዕጣን መሠዊያውን፣ [28]የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያውንና ዕቃዎቹን ሁሉ እንዲሁም የመታጠቢያ ሰኑን ከነመቆሚያው እንድትቀባበት ይሁን:: [29]እጅግ የተቀደሱ ይሆኑም ዘንድ ቀድሳቸው፤ የሚነካቸውም ሁሉ የተቀደሰ ይሆናል:: [30]ካህናት ሆነው ያገለግሉኝ ዘንድ አሮንና ወንዶች ልጆቹን ቅባቸው፤ ቀድሳቸውም:: [31]ለእስራኤላውያን ንገራቸው፤ 'በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ ይህ የእኔ የተቀደሰ የቅብዐት ዘይት ይሆናል፤ [32]በማንም ሰው ሰውነት ላይ አታፍስሱት፤ በተመሳሳይ መንገድ ምንም ዘይት አትሥሩ፤ የተቀደሰ ነው፤ ቅዱስ መሆኑን ልብ በሉ:: [33]ተመሳሳይ ዐይነት የሠራና ከካህናት ሌላ በማንም ሰው ላይ ያፈሰሰ ሁሉ ከወገኑ ይወገድ::

## ዕጣን

[34]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ "ተመጣጣኝ በማድረግ የጣፋጭ ሽቱ ቅመሞች፣ የሚንጠባጠብ ሙጫ፣ በዛጐል ውስጥ የሚገኝ ሽቱ፣ የሚሸት ሙጫ፣ እና ንጹሕ ዕጣን ወስደህ [35]በቀማሚ እንደ ተሠራ ጣፋጭ መዐዛ ያለው የተቀመመ ዕጣን አብጅ፤ በጨው የተቀመመ፣ ንጹሕና የተቀደሰ ይሁን:: [36]ከእርሱም ጥቂቱን ወቅጠህ ዱቄት በማድረግ አልመህ በመገናኛው ድንኳን ከምስክሩ ፊት ለፊት ከአንተ ጋር በምገናኝበት ስፍራ አስቀምጠው፤ ለአንተ እጅግ የተቀደሰ ይሆናል:: [37]ለራስህ በዚያ ዐይነት መንገድ ምንም ዐይነት ዕጣን አታብጅ:: ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የተቀደሰ መሆኑን ልብ በል:: [38]በመልካም ሽታው ይደሰት ዘንድ እርሱን አስመስሎ የሚሠራ ሁሉ ከወገኑ የተወገደ ይሁን::

## ባስልኤልና ኤልያብ

31፥2-6 ተጓ ምብ - ዘፀ 35፥30-35

**31** ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]"እነሆ፣ ከይሁዳ ነገድ የሆር የልጅ ልጅ የሆነውን የኡሪን ልጅ ባስልኤልን መርጬዋለሁ:: [3]በሁሉም ዐይነት የእጅ ጥበብ ሥራ፣ ብልሃት፣ ችሎታና ዕውቀት እንዲኖረው የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም) መንፈስ ሞልቼዋለሁ፤ [4]ይኸውም በወርቅ፣ በብርና በናስ ለሚሠሩት ሥራዎች በጥበብ የተሠሩ ጌጦችን እንዲያበጅ፣ [5]ድንጋዮችን እንዲቀርጽና እንዲጠርብ ከእንጨትም ጥርብ እንዲያወጣ፣ ሁሉንም ዐይነት የእጅ ጥበብ ሥራዎችን እንዲያከናውን ነው:: [6]በተጨማሪም ከዳን ነገድ የሆነውን የአሂሳማክን ልጅ ኤልያብን እንዲረዳው መርጬዋለሁ፤ እንዲሁም ያዘዝሁህን ሁሉ

[a]23 ወደ 6 ኪሎ ግራም ያህል ነው::
[b]24 ወደ 4 ሊትር ያህል ነው::

30፥14 ዘፀ38፥26፤ ዘኍ1፥3፡18፤14፥29፤ 26፥2፤32፥11፤ 2ዜና25፥5
30፥15 ምሳ22፥2፤ ኤፌ6፥9
30፥16 ቍ12፤ ዘፀ38፥25-28፤ 2ዜና24፥5፤ ዘኍ31፥54
30፥18 ዘፀ31፥9፤ 35፥16፤38፥8፤ 39፥39፤40፥7፡30፤ 1ነገ7፥38፤2ዜና4፥6
30፥19 ዘፀ29፥4፤ 40፥12፡31-32፤ዘሌ 8፥6፤መዝ26፥6፤ዮሐ 13፥10፤ዕብ10፥22
30፥20 ዘፀ28፥43
30፥21 ዘፀ27፥21፤ 29፥42
30፥23 ዘፍ43፥11፤ 37፥25፤ምሳ7፥17፤ ማሕ4፥14፤ኢሳ43፥24 ፤ኤር6፥20
30፥24 ቍ13፤መዝ 45፥8፤ሕዝ27፥19
30፥25 ቍ35፤ዘፀ 29፥7፤37፥29፤ዘኍ 9፥30፤1ሳሙ9፥16
30፥26 ዘፀ40፥9፤ ዘሌ8፥10፤ዘኍ7፥1
30፥29 ዘፀ29፥37፤ ዘሌ6፥18፡27፤8፥10- 11፤ማቴ23፥17
30፥30 ዘፀ28፥41፤ 29፥7፤ዘሌ8፥2፡12፡ 30፤10፥7፤16፥32፤ 21፥10፡12፤ዘኍ15፥ 12፤መዝ133፥2
30፥31 ዘፀ29፥7:42
30፥32 ቍ25:37
30፥33 ቍ38፤ ዘፍ17፥14
30፥34 ማሕ3፥6
30፥35 ቍ25፤ ዘፀ25፥6
30፥36 ቍ32፤ ዘፀ25፥22፤29፥37፤ ዘሌ2፥3
30፥37 ቍ32
30፥38 ቍ33
31፥2 ዘፀ17፥10፤ 36፥1፡2፤37፥1፤ 38፥22፤1ዜና2፥20፤ 2ዜና1፥5
31፥3 ዘፀ28፥3፤ 1ነገ7፥14፤1ቆሮ12፥4
31፥6 ዘፀ28፥3፤ 36፥1፡2፤38፥23፤ 1ነገ7፥14፤2ዜና2፥14

ከተወሳው መርሕ ጋር የሚያያዝ ነው፤ (የ13፥13 ማብ ይመ)::

30፥14 *ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከሃያ በላይ ሆኖ፤* ለውትድርና የሚመለመልበት (የሚመረጥበት) ዕድሜ ነው፤ (ዘኍ 1፥3 ይመ)::

30፥16 *ለመገናኛው ድንኳን፤* የ27፥21 ማብ ይመ::

30፥18 *ለመታጠቢያ ከናስ ... የናስ ሰን (ጸሕል)፤* እስራኤላውያን ሴቶች ከሰጡት የናስ መስተዋት የሚሠራ ነው፤ (38፥8 ይመ):: *መታጠቢያ፤* የ29፥4 ማብ ይመ::

30፥23-24 *ከርቤ ... ቀረፋ ... ጠጅ ሣር ... ብርጕድ፤* የ25፥6 ማብ ይመ::

30፥33 *ከወገኑ ይወገድ፤* የ12፥15 ማብ ይመ::

30፥34 *የሚንጠባጠብ ሙጫ፣ በዛጐል ውስጥ የሚገኝ ሽቱ፣ የሚሸት ሙጫ፤* የ25፥6 ማብ ይመ:: *ጣፋጭ ... ንጹሕ ዕጣን፤* በደቡብ ዐረቢያ የሚበቅል የዛፍ ቅርፊት ነው::

31፥2 *ባስልኤል፤* "በእግዚአብሔር ጥላ/ጥበቃ ውስጥ ያለ" ማለት ነው:: *ሆር፤* የ17፥10 ማብ ይመ::

31፥3 *የእግዚአብሔርን መንፈስ ሞልቼዋለሁ፤* በልዩ ጥበብና ችሎታ በእጅ ሙያ መሥራት መንፈሳዊ ስጦታ ሲሆን፣ ይህም አንድን ሰው ለእግዚአብሔር አገልግሎት ያደርገዋል::

31፥6 *ኤልያብ፤* "አባቴ (መለኮታዊው) ድንኳኔ/ማደሪያዬ"

ያደርጉ ዘንድ ለእጅ ጥበብ ዐዋቂዎች ሁሉ ብልሃትን ሰጥቻቸዋለሁ፤ [7]ይኸውም የመገናኛውን ድንኳን፣ የምስክሩን ታቦት በላዩ ላይ ካለው ከስርየት መክደኛው ጋር፣ ሌሎች የድንኳኑን መገልገያ ዕቃዎች ሁሉ፣ [8]ጠረጴዛውን ከነዕቃዎቹ፣ ከንጹሕ ወርቅ የተሠራውን የወርቅ መቅረዝ ከነዕቃዎቹ፣ የዕጣኑን መሠዊያ፣ [9]የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያውን ከነዕቃዎቹ፣ ሰኑን፣ ከእነማስቀመጫው፣ [10]ከፈትል የተሠሩ ልብሶችን ይኸውም የካህኑን የአሮንን የተቀደሱ ልብሶችንና ካህናት ሆነው ሲያገለግሉ የሚለብሷቸው የወንድ ልጆቹ ልብሶችን፣ [11]እንዲሁም የመቅደሱ የሆነውን ቅብዐ ዘይትና ጣፋጭ ሽታ ያለውን ዕጣን እንዲሠሩ ነው፤ ልክ እኔ እንዳዘዝሁህ ያብጁአቸው።

## ሰንበት

[12]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [13]“ለእስራኤላውያን ንገራቸው፤ ‘ሰንበቴን አክብሩ፤ ይህም በእኔና በእናንተ መካከል በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ ምልክት ይሆናል፤ ይኸውም የምቀድሳችሁ[*] እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንደ ሆንሁ እንድታውቁ ነው።

[14]“ለእናንተ ቅዱስ ነውና ሰንበትን አክብሩ፤ ማንም ቢሽረው በሞት ይቀጣል፤ በዚያ ቀን ማንም የሚሠራ ቢኖር ከወገኑ ተነጥሎ ይለይ። [15]ስድስት ቀን ሥራ ይሠራል፤ ሰባተኛው ቀን ግን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የተቀደሰ የዕረፍት ሰንበት ነው፤ በሰንበት ቀን ማንም ቢሠራ በሞት መቀጣት አለበት። [16]እስራኤላውያን በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ ሰንበትን በመጠበቅ የዘላለም ኪዳን አድርገው ማክበር አለባቸው፤ [17]በእኔና በእስራኤላውያን መካከል ለዘላለም ምልክት ይሆናል፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሰማይንና ምድርን በስድስት ቀን ሠርቶ፣ በሰባተኛው ቀን ከሥራ ታቅቦ ዐርፎአልና።’ ”

[18]እግዚአብሔር (ያህዌ) በሲና ተራራ ላይ ለሙሴ መናገሩን ከፈጸመ በኋላ፣ በእግዚአብሔር (ኤሎሂም) ጣት የተጻፈባቸውን የድንጋይ ጽላቶች፣ ሁለቱን የምስክር ጽላቶች ለእርሱ ሰጠው።

## የወርቅ ጥጃ

**32** ሕዝቡ ሙሴ ከተራራው ላይ ሳይ ወርድ ብዙ እንደ ቆየ ባዩ ጊዜ፣ ወደ አሮን ተሰብስበው፣ “ና፣ በፊታችን የሚሄዱ አማልክት[*] ሥራልን፤ ያ ከግብፅ ያወጣን ሙሴ ምን እንዳገኘው አናውቅም” አሉት።

[2]አሮንም፣ “የሚስቶቻችሁን፣ የወንድና የሴት ልጆቻችሁን የጆሮ ወርቅ አውልቃችሁ ወደ እኔ አምጡ” ብሎ መለሰላቸው። [3]ሕዝቡም ሁሉ የጆሮ ወርቃቸውን አውልቀው ወደ አሮን አመጡ። [4]እርሱም የሰጡትን ወስዶ በመሣሪያ በመቅረጽ በጥጃ ምስል ጣዖት አድርጎ ሠራው፤ ከዚያም እነርሱ፣ “እስራኤል ሆይ፤ ከግብፅ ያወጡህ አማልክት[*] እነዚህ ናቸው” አሉ።

[5]አሮን ይህን ባየ ጊዜ በወርቅ ጥጃው ፊት ለፊት መሠዊያ ሠርቶ፣ “ነገ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በዓል ይሆናል” ብሎ ዐወጀ። [6]በማግሥቱ ሕዝቡ በማለዳ ተነሥተው የሚቃጠል መሥዋዕት ሠዉ፤ የኅብረት መሥዋዕት[*] አቀረቡ፤ ከዚህም በኋላ ይበሉና ይጠጡ ዘንድ ተቀመጡ፤ ሊዘፍኑም ተነሡ።

31፥7 ዘፀ36፥8-38፤ 37፥1-5፡6፤40፥20
31፥8 ዘፀ37፥10-16፤17-24፤ዘሌ24፥4፤ 37፥25-28
31፥9 ዘፀ30፥18፤ 38፥3፤ዘኍ4፥14
31፥10 ዘፀ28፥2
31፥11 ዘፀ30፥22-32፤37፥29፤25፥6፡9
31፥13 ቍ 17፤ዘፀ 20፥8፤29፥42፤ዘሌ 11፥44፤20፥8፤21፥8፤ ኢሳ56፥4፤ሕዝ20፥12 ፡20፤37፥28
31፥14 ዘፀ35፥2፤ ዘኍ15፥32-36
31፥15 ዘፍ 2፥3፤ ዘፀ20፥8-11፤35፥2፤ ዘሌ16፥29፤23፥3፤ ዘኍ29፥7
31፥16 ዘፀ20፥8
31፥17 ቍ 13፤ ዘፍ2፥2-3፤ዘፀ20፥9፤ ኢሳ56፥2፤58፥13፤ 66፥23፤ኤር17፥21-22፤ሕዝ20፥12፡20
31፥18 ዘፀ19፥11፤ 24፥12፤32፥15-16፤ 34፥1፡28፤ዘዳ4፥13፤ 9፥10፤2ቆሮ3፥3፤ ዕብ9፥4
32፥1 ቍ 23፤ዘፍ 7፥4፤ዘፀ13፥21፤ዘዳ 9፥9-12፤ሐሥ7፥40
32፥2 መሳ8፥24-27
32፥4 ቍ 8፡24፡35፤ ዘፀ20፥23፤ዘዳ9፥16፤ መሳ17፥3-4፤1ነገ12፥ 28፤14፥9፤2ነገ10፥29 ፤17፥16፤2ዜና13፥8፤ ነህ9፥18፤መዝ106፥ 19፤ኢሳ30፥22፤ 42፥17፤ሆሴ8፥6፤ 10፥5፤ሐሥ7፥41
32፥5 ዘሌ23፥2፡ 37፤2ነገ10፥20፤ ኢል2፥15
32፥6 ቍ 17-19፤ ዘፀ20፥24፤34፥15፤

[*]13 ወይም፣ *ቅዱስ አድርጌ የምለያችሁ* ተብሎ መተርጐም ይችላል።

[*]1 በዚህ እንዲሁም በቍጥር 23 እና 31 ላይ *አምላክ* ተብሎ መተርጐም ይችላል።

[*]4 በዚህና በቍጥር 8 ላይ፣ *ይህ አምላካችሁ ነው* ተብሎ መተርጐም ይችላል።

[*]6 በትውፊት፣ *የሰላም መሥዋዕት* በመባል ይታወቃል።

ነው” ማለት ነው። ባስልኤልና (የቍ 2 ማብ ይመ) ኤልያብ የሚሉት ስሞች የመገናኛውን ድንኳን ለመሥራት የሚያስፈልጉትንና ታላቅ ችሎታ ያላቸውን ሰዎች በሚገባ የሚገልጹ ናቸው።

31፥7 *የመገናኛውን ድንኳን፤* የ27፥21 ማብ ይመ።

31፥13 *ሰንበቴን አክብሩ፤* የመገናኛውን ድንኳንና የካህናቱን ልብስ ለመሥራት የተሰጠው መመሪያ የተደመደመው እስራኤላውያን ከእግዚአብሔር የተሰጣቸውን ተልዕኮ በሚፈጽሙበት ጊዜ እንኳ ሰንበትን የመጠበቅ ኀላፊነት እንዳለባቸው በማስገንዘብ ነው።

31፥14 *ከወገኑ ተነጥሎ፤* የ12፥15 ማብ ይመ።

31፥16-17 *ኪዳን ... ምልክት፤* እስራኤል በማያቋርጥ ተግባሯና በእግዚአብሔርም አገልግሎት በዓላት ዕረፍት እግዚአብሔር በፍጥረት ጊዜ ያከናወናቸውን ተግባራት እንደ ምሳሌ በመከተል ከእግዚአብሔር ጋር የገባችውን ቃል ኪዳን ዘወትር መጠበቅ አለባት፤ (የዘፍ 9፥12 ማብ ይመ)።

31፥18 *ሁለቱን ... ጽላቶች፤* እንደ ጥንት መካከለኛው ምሥራቅ ልማድ ሁሉ፣ እነዚህም ጽላቶች የዐሥርቱ ትእዛዛት ሁለት ክፍሎች ሳይሆኑ የቃል ኪዳኑ ቅጆች ናቸው። እያንዳንዱ ቃል ኪዳን ተጋቢ ወገን የየራሱ አንድ ቅጅ ይኖረዋል። በልማዱ መሠረት ለእስራኤል የሚሰጠው ቅጂ በአምላኳ ፊት የሚቀመጥ ሲሆን፣ ሁለቱም ጽላቶች (ለእግዚአብሔርና ለእስራኤል የሚሰጠው) በታቦቱ ውስጥ እንዲቀመጡ ይደረጋል (25፥21 ይመ)። *ምስክር፤* የ16፥34፡25፥16 ማብ ይመ። *በእግዚአብሔር ጣት የተጻፈባቸው፤* ምክንያቱም የእግዚአብሔር ቃል ኪዳን ነው፤ (19፥5-6 ይመ)፤ የኪዳኑም ስምምነቶች የእርሱ ናቸው፤ (20፥1-7)።

32፥1 *ብዙ ...ጊዜ፤* አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ማለት ነው፤ (24፥18 እና ማብ ይመ)፤ *ያ ከግብፅ ያወጣን ሙሴ፤* የእስራኤል የኪዳን አምላክ በቸርነቱ ያደረገውን ታምር የሚፃረር አባባል ነው፤ (20፥2 እና ማብ እንዲሁም 29፥46 ይመ)።

32፥2 *የጆሮ ወርቅ፤* ምናልባት ከግብፅ በዝብዘው ያመጡት ሳይሆን አይቀርም፤ (3፥21-22፡11፥2-3፡12፥35-36 ይመ)።

32፥4 *በመሣሪያ በመቅረጽ በጥጃ ምስል ሠራው፤* ከዕንጨት ተጠርቦ የተሠራና በወርቅ የተለበጠ (በኋላ ላይ በእሳት እንዲቃጠል ተደርጓል፤ ቍ 20) ወይም ከወርቅ ተጠፍጥፎ የተሠራና በቅርጽ መሥሪያ መሣሪያ የተበጀ ሊሆን ይችላል። ይህ ጥጃ ከግብፃውያን አጲስ የጥጃ አምላክ ቅርጽ ጋር ተመሳሳይነት ያለው ሳይሆን አይቀርም፤ (የኤር 46፥15 ማብ ይመ)። እስራኤላውያን እንዲህ ያለውን ጥጃ በመሥራታቸው ሁለተኛውን ትእዛዝ በግልጽ ተላልፈዋል፤ (20፥4-5)። ከግብፅ ምድር መርቶ ያወጣህ አምላክህ ይህ ነው፤ በ20፥2 ላይ የተጠቀሰውን የሚያሽሟጥጥ አነጋገር ነው። ከምእተ ዓመታት በኋላ ንጉሥ ኢዮርብዓም በሰሜናዊው የእስራኤል መንግሥት ሁለት የወርቅ ጥጃዎች ሠርቶ ባቆመ ጊዜ እነዚህን ቃሎች ጠቅሶ ነበር (1ነገ12፥28-29)።

32፥5 *በወርቅ ጥጃው ፊት ለፊት መሠዊያ ... ለእግዚአብሔር በዓል፤* ከሁኔታው እንደምንረዳው አሮን ጣዖት ማምለክ የሚያስከትለውን ጣጣ ስለ ተረዳ ሕዝቡ ፊቱን ከእግዚአብሔር ፈጽሞ እንዳይመለስ ፈጣን እርምጃ ወሰደ።

32፥6 *ተቀመጡ፤ ሊዘፍኑም ተነሡ፤* ይህ ድርጊት ጣዖት አምላኪነትን የሚያሳይ የአምልኮተ ጣዖት ምልክት ነው። ጳውሎስ ይህን ዐረፍተ ነገር በመጥቀስ የእስራኤልን ጣዖት አምላኪነት በግልጽ አሳይቷል፤ (1ቆሮ 10፥7 ይመ)። “ሊዘፍኑም ተነሡ”

[7]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "ከግብፅ ያወጣኻቸው ሕዝብህ ስተዋልና ውረድ አለው፤ [8]ካዘዝኋቸው ፈቀቅ ለማለት ጊጣኖች ሆኑ፤ ለራሳቸውም በጥጃ ምስል የተቀረጸ ጣዖትን ሠሩ፤ ለእርሱም ሰገዱለት፤ ሠዉለትም፤ እንዲሁም፣ 'እስራኤል ሆይ፤ ከግብፅ ምድር ያወጡህ አማልክትህ እነዚህ ናቸው' አሉ::

[9]እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "እነዚህን ሕዝብ አይቻቸዋለሁ፤ አንገተ ደንዳናዎችም ናቸው፤ [10]አሁንም በእ ነርሱ ላይ፣ ቍጣዬ እንዲነድና እንዳጠፋ ቸው ተወኝ፤ ከዚያም አንተን ለታላቅ ሕዝብ አደርግሃለሁ::"

[11]ነገር ግን ሙሴ የአምላኩን የእግዚአ ብሔርን (ኤሎሂም ያህዌ) ቸርነት ፈለገ፤ እንዲህም አለ፤ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ በታላቅ ሥል ጣንህና በኀያል ክንድህ ከግብፅ ባወጣኸው ሕዝብህ ላይ ቍጣህ ለምን ይነዳል? [12]ግብፃውያን፣ 'በተራራዎቹ ላይ ሊገድላቸው ከገጸ ምድርም ሊያጠፋቸው ስለ ፈለገ ነው ያወጣቸው' ለምን ይበሉ? ከክፉ ቍጣህ ተመለስ፤ ታገሥ፤ በሕዝብህም ላይ ጥፋት አታምጣ:: [13]ለባሪያዎችህ ለአብርሃም፣ ለይስሐ ቅና ለእስራኤል፣ 'ዘርህን እንደ ሰማይ ከዋ ክብት አበዛዋለሁ፤ ለዘርህም ተስፋ አድርጌ የሰጠኋቸውን ይህችን ምድር ሁሉ እሰጣ ቸዋለሁ፤ ለዘላለምም ርስታቸው ትሆናለች' በማለት በራስህ የማልኸውን አስታውስ::" [14]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ታገሠ፤ በሕዝ ቡም ላይ አመጣባቸዋለሁ ያለውን ጥፋት አላመጣባቸውም::

[15]ሙሴም ሁለቱን የምስክር ጽላቶች በእጆቹ ይዞ ከተራራው ወረደ፤ ጽላቶቹም ከፊትና ከኋላ በሁለት ወገን ተጽፎባቸው ነበር:: [16]ጽላቶቹ የእግዚአብሔር ሥራ ነበሩ፤ በጽላቶቹ ላይ የተቀረጸ ጽሕፈትም የእግዚ አብሔር (ያህዌ) ጽሕፈት ነበር::

[17]ኢያሱ የሕዝቡን የጩኸት ድምፅ በሰማ ጊዜ ሙሴን፣ "በሰፈሩ ውስጥ የጦርነት ድምፅ አለ" አለው:: [18]ሙሴም

"የድል ድምፅ አይደለም፤
የሽንፈትም ድምፅ አይደለም፤
የምሰማው የዘፈን ድምፅ ነው"
ብሎ መለሰለት::

[19]ሙሴ ወደ ሰፈሩ ደርሶ ጥጃውንና ጭፈራውን ባየ ጊዜ ቍጣው ነደደ፤ ጽላቶ ቹን ከእጁ በመወርወር ከተራራው ግርጌ ሰባበራቸው:: [20]የሠሩትን ጥጃ ወስዶ በእ ሳት አቃጠለው፤ ከዚያም ዱቄት እስኪሆን ፈጨው፤ በውሃ ላይ በተነው፤ እስራኤላው ያንም እንዲጠጡት አደረገ::

[21]አሮንንም፣ "ወደዚህ አስከፊ ኀጢአት ትመራቸው ዘንድ ይህ ሕዝብ ምን አደ ረገህ?" አለው::

[22]አሮንም መለሰ፣ "ጌታዬ ሆይ አትቈጣ ብሎ መለሰለት፤ ይህ ሕዝብ ሁልጊዜ ለክፋት ያዘነበለ መሆኑን አንተ ታው ቃለህ፤ [23]እነርሱም 'በፊታችን የሚሄዱ አማ ልክት ሥራልን፤ ይህ ከግብፅ ያወጣን ሙሴ ምን እንዳገኘው አናውቅም' አሉኝ:: [24]ስለ ዚህ፣ 'ማንኛውም ዐይነት የወርቅ ጌጣጌጥ ያለው ሁሉ ያውልቀው' አልኋቸው፤ ከዚ ያም ወርቁን ሰጡኝ፤ ወደ እሳቱ ጣልሁት፤ ይህም ጥጃ ወጣ::"

[25]ሕዝቡ ከቍጥጥር ውጭ እንደ ሆኑ፣ አሮ ንም መረን እንደ ለቀቃቸውና በጠላቶቻቸውም

ዘሌ3፥1፤4፥10፤6፥12፤ 9፥4፤22፥21፤ዘኍ6፥ 14፤25፥2፤ዘዳ27፥7፤ መሳ20፥26፤መሳ19፥ 4፤ሩት3፥3፤ 1ሳሙ 1፥9፤2ሳሙ11፥11፤ 1ነገ13፥23፤18፥42፤ ነህ8፥12፤ኢዮ1፥4፤ መክ5፥18፤8፥15፤ ኤር16፥8፤ሕዝ43፥27 ፤ሐሥ7፥41፤ 1ቆሮ10፥7፤
32፥7 ቍ4:11፤ ዘፍ6፥11-12፤ ዘፀ33፥11፤ሕዝ20፥8
32፥8 ቍ4፤ዘፀ 20፥4፤22፥20፤1ነገ 12፥28፤ኤር7፥26፤ 16፥12፤ሕዝ23፥8፤ ሚል2፥8፤3፥7
32፥9 ዘፀ33፥3:5፤ 34፥9፤ዘዳ9፥6:13፤ 10፥16፤31፥27፤መሳ 2፥19፤2ነገ17፥14፤ 2ዜና30፥8፤36፥13፤ ነህ9፥16፤መዝ78፥8፤ ምሳ29፥1፤ኢሳ46፥12 ፤48፥4፤ኤር7፥26፤ ሕዝ2፥4፤ሆሴ4፥16፤ ሐሥ7፥51
32፥10 ዘፀ22፥24፤ 33፥3-5፤ዘኍ14፥12፤ 16፥21:45፤ዘዳ9፥14 :19፤1ሳሙ2፥25፤ መዝ106፥23፤ኤር 7፥16፤11፥14፤14፥11 :12፤ሕዝ20፥13
32፥11 ቍ13፤ዘዳ 9፥18:26፤1ሳሙ7፥9፤ 2ሳሙ21፥1፤ 2ዜና 15፥2፤1ነህ1፥10፤ መዝ9፥10፤34፥4፤10 6፥23፤136፥12፤ኢሳ 9፥13፤ኤር15፥
32፥12 ቍ14፤ዘፀ 33፥13፤ ዘኍ14፥13-16፤ ዘዳ9፥28
32፥13 ዘፍ12፥7፤ 15፥5፤22፥7:16:17፤ ዘፀ2፥24፤33፥13፤ዕብ 6፥13
32፥14 ዘዳ9፥19፤ 1ሳሙ15፥11፤ 2ሳሙ24፥16፤ 1ነገ21፥29፤1ዜና21፥15፤መዝ106፥45፤ኤር18፥8፤26፥3:19፤አሞ7፥3: 6፤ ዮና3፥10
32፥15 ዘፀ19፥18፤31፥18፤34፥4:29፤ዘዳ9፥15፤ 2ቆሮ3፥3፤ዕብ9፥4
32፥16 ዘፀ24፥12
32፥17 ዘፀ17፥9
32፥19 ቍ6፤ዘፀ34፥1፤ ዘዳ9፥16:17፤ዕዝ9፥3፤መዝ119፥53:158፤ 1ቆሮ10፥7
32፥20 ዘዳ7፥25፤ 9፥21፤12፥3፤ኢሱ7፥1፤2ነገ23፥6፤ 1ዜና14፥12፤ 2ዜና34፥7፤ሚክ1፥7
32፥22 ዘፍ18፥30፤ዘዳ9፥24፤ 28፥20፤2ነገ 21፥15፤ዕዝ9፥13፤ነህ9፥28፤ኤር4፥4፤44፥3፤ሕዝ6፥9
32፥23 ቍ1፤ሐሥ7፥40
32፥24 ቍ4
32፥25 ዘፍ38፥23

ለሚለው ሐረግ የገባው የዕብራይስጡ ግሥ አብዛኛውን ጊዜ ሩካቤአዊ ወይም ተዋስቦአዊ ትርጕም አለው፤ (ዘፍ 26፥8 ይመ):: በጥንት ዘመን የአረማውያን (የጣዖት አምላኪዎች) አምልኮ በሩካቤ ሥጋ የታጀበ ነው::

32፥7:9 *ሕዝብህ ... እነዚህን ሕዝብ፤* እግዚአብሔር እስራኤልን "ሕዝቤ" (በ3፥10 ላይ እንደተጠቀሰው) ብሎ ያልጠራ እስራኤል ከእግዚአብሔ ጋር የገባችውን ቃል ኪዳን በማፍረስ ሲሆን ይህም ድርጊቷ በእግዚአብሔር የተካደች እንድትሆን አድርጓታል::

32፥7 *ስተዋል፤* ስለዚህ ለፍርድ ተቃርበዋል፤ (ቍ 10፤ ዘፍ 6፥11-13 ይመ)::

32፥9 *አንገተ ደንዳናዎች፤* እንደ ዓመፀኛ በሬና ፈረስ ማለት ነው፤ (ኤር 27:11-12፤ የነህ 3፥5 ማብ ይመ)::

32፥10 *ከዚያም አንተን ለታላቅ ሕዝብ አደርግሃለሁ፤* የአብርሃም ዘር የሆኑት እስራኤላውያን ከጠፉ በኋላ፣ እግዚአብሔር ለአብርሃም የገባውን ቃል ኪዳን ወደ ሙሴ ያዞራል፤ (ዘፍ 12፥2 ይመ)::

32፥11 *ሕዝብህ፤* ሙሴ እግዚአብሔር ራሱ የተናገረውን ቃል ከጠቀሰ በኋላ (ቍ 7 እና ማብ ይመ) እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር ያለውን ግንኙነት እንዲመለከትና ከዚያም ስሙን በግብፃውያን ፊት ከፍ ከፍ እንዲያደርግ (ቍ 12 ይመ) በመጨረሻም ለእስራኤል አባቶች የገባውን ቃል ኪዳን እንዲያስታውስ ያሳስበዋል (ቍ 13 ይመ)::

32፥13 *ለእስራኤል፤* ለያዕቆብ ለማለት ነው፤ (33፥1፤ ዘፍ 32፥28 ይመ)::

32፥14 *እግዚአብሔር ታገሠ፤* የኤር 18፥7-10 ማብ፤ 2ሳሙ 24፥16፤ መዝ 106፥45፤ አሞ 7፥1-6፤ ያዕ 5፥16 ይመ)::

32፥15 *ከተራራው ወረደ፤* 24፥18 እና ማብ ይመ:: *ሁለቱን ... ጽላቶች፤* 31፥18 እና ማብ ይመ:: *የምስክር፤* የ16፥34 ማብ እና 25፥16 ይመ:: ከፊት ከኋላ በሁለት በኩል ተጽፎባቸው ነበር፤ በጥንት ዘመን በጽላቶች ላይ የሚጻፈው በሁለቱም በኩል ነበር::

32፥16 *በጽላቶቹ ላይ የተቀረጸው ጽሕፈትም የእግዚአብሔር ጽሕፈት ነበር፤* 31፥18 ይመ::

32፥17 *ኢያሱ፤* ምናልባት ሙሴ ወደ ተራራው ሲወጣ እስከ ግማሽ ድረስ ሳይሸኘው አይቀርም፤ (24፥13 ይመ)

32፥19 *ጽላቶቹን ከእጁ በመወርወር ከተራራው ግርጌ ሰባበራቸው፤* እስራኤላውያን የገቡትን ቃል ኪዳን እንዳፈረሱ የሚያሳይ ድርጊት ነው::

32፥20 *በእሳት አቃጠለው ... ዱቄት እስኪሆን ፈጨው፤* በቤቴል የሚገኘው የንጉሥ ኢዮርብዓም መሠዊያ ተመሳሳይ ዕጣ ደርሶበታል (የቍ 4 ማብ እና 2ነገ 23፥15 ይመ)::

*32፥22-24፤* አሮን እጅግ ስለፈራ በሕዝቡ አሳበበ፤ (የዘፍ 3፥12-13 ማብ ይመ)::

32፥24 *ይህም ጥጃ ወጣ፤* አሮን እንዲህ የመሰለውን አስደናቂ ታሪክ ሲያቀናብር ሙሴ አያምነኝም ብሎ ከቶ አላሰበም::

32፥25 *መረን እንደ ለቀቃቸው፤* ምሳ 29፥18 ይመ:: እግዚአብሔርን መታዘዝና ማምለክ በተው ሕዝብ መካከል ሥርዐት

ዘንድ መሳለቂያ እንደ ሆኑ ሙሴ አስተዋለ። [26]ስለዚህ በሰፈሩ መግቢያ ላይ ቆሞ፣ "የእግዚአብሔር (ያህዌ) የሆነ ሁሉ ወደ እኔ ይምጣ" አለ፤ ሌዋውያኑም ሁሉ ከእርሱ ጋር ሆኑ።

[27]ከዚያም፣ "የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚለው ይህ ነው፤ 'እያንዳንዱ ሰው በወገቡ ላይ ሰይፍ ይታጠቅ፤ በሰፈር ውስጥ ከዳር እዳር እየተመላለሰ እያንዳንዱ ወንድሙን፣ ጓደኛውንና ጎረቤቱን ይግደል'" አላቸው። [28]ሌዋውያኑ ሙሴ እንዳዘዛቸው ፈጸሙ፤ በዚያኑም ዕለት ከሕዝቡ ሦስት ሺህ ያህል አለቀ። [29]ከዚያም ሙሴ፣ "በራሳችሁ ወንዶች ልጆችና ወንድሞች ላይ በመነሣታችሁ፣ በዛሬዋ ቀን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የተለያችሁ ሆናችኋል፤ በዛሬዎም ዕለት ባርኳችኋል" አለ።

[30]በማግሥቱም ሙሴ ሕዝቡን፣ "እጅግ የከፋ ኀጢአት ሠርታችኋል፤ አሁን ግን ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) እወጣለሁ፤ ምናልባት ኀጢአታችሁን ማስተስረይ እችል ይሆናል" አላቸው።

[31]ስለዚህ ሙሴ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ተመልሶ እንዲህ አለው፤ "ወዮ እነዚህ ሕዝብ የሠሩት ምን ዐይነት የከፋ ኀጢአት ነው! ለራሳቸውም የወርቅ አማልክት ሠሩ። [32]አሁን ግን እባቱ ኀጢአታቸውን ይቅር በል፤ ያለዚያ ግን ከጻፍኸው መጽሐፍ እኔን ደምስሰኝ።" [33]እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ እንዲህ ሲል መለሰለት፤ "የበደለኝን ሁሉ ከመጽሐፌ እደመስሰዋለሁ፤ [34]አሁን ሂድ፤ ሕዝቡን ወደ ተናገርኩት ስፍራ ምራው፤ መልአኬም በፊትህ ይሄዳል፤ ሆኖም የምቀጣበት ጊዜ ሲደርስ፣ ስለ ኀጢአታቸው እቀጣቸዋለሁ።"

[35]አሮን በሠራው ጥጃ ባደረጉት ነገር እግዚአብሔር (ያህዌ) ሕዝቡን በመቅሠፍት መታ።

32፥27 ዘኍ25፥3፡5፤ዘዳ33፥9፤ሕዝ9፥5
32፥30 ዘሌ1፥4፤4፥20፡26፤5፥6፡10፡13፤6፥7፤1ሳሙ12፥20፤መዝ25፥11፤85፥2
32፥31 ዘፀ20፥23፤34፥9፤ዘዳ9፥18
32፥32 ዘኍ14፥19፤መዝ69፥28፤ሕዝ13፥9፤ዳን7፥10፤12፥1፤ሚል3፥16፤ሉቃ10፥20፤ሮሜ9፥3
32፥33 ዘፀ17፥14፤ኢዮ21፥20፤ራእ3፥5
32፥34 ዘፍ50፥19፤ዘፀ3፥17፤14፥19፤15፥17፤ዘዳ32፥35፤መዝ89፥32፤94፥23፤99፥8፤109፥20፤ኢሳ27፥11 ኤር5፥9፤11፥22፤23፥2፤44፥13፡29፤ሆሴ12፥2፤ሮሜ2፥5-6
32፥35 ቍ4
33፥1 ዘፍ12፥7፤ዘፀ13፥11፤ዘኍ14፥23፤ዕብ6፥13
33፥2 ዘፀ14፥19፤23፥28
33፥3 ዘፀ3፥8፤32፥9፡10፤ሐሥ7፥51
33፥4 ዘኍ14፥39፤ሕስ4፥1፤ዕዝ9፥3፤መዝ119፥53
33፥5 ዘፀ32፥9፡10
33፥6 ዘፀ3፥1
33፥7 ዘፍ25፥22፤ዘፀ27፥21፤1ነገ22፥5
33፥8 ቍ10፤ዘኍ16፥27
33፥9 ዘፀ13፥21፤19፥9፤29፥42፤31፥18፤ዘዳ31፥15፤1ቆሮ10፥1፤መዝ99፥7

# 33

ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ "አንተና ከግብፅ ያወጣኸው ሕዝብህ ይህን ስፍራ ለቃችሁ 'ለዘርህ እሰጣለሁ' በማለት ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ በመሐላ ተስፋ ወደ ገባሁላችሁ ምድር ሂዱ። [2]መልአክን በፊትህ በመላክ፣ ከነዓናውያንን፣ አሞራውያንን፣ ኬጢያውያንን፣ ፌርዛውያንን፣ ኤዊያውያንንና ኢያቡሳውያንን አስወጣለሁ። [3]ማርና ወተት ወደምታፈሰው ምድር ውጡ፤ ነገር ግን አንገተ ደንዳና ሕዝብ ስለሆናችሁ፣ በመንገድ ላይ እንዳላጠፋችሁ እኔ ከእናንተ ጋር አልሄድም።"

[4]ሕዝቡም እነዚህን አሳዛኝ ቃላት በሰሙ ጊዜ ይተክዙ ጀመር፤ ማንም ሰው አንዳች ጌጥ አላደረገም። [5]እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን፣ "እስራኤላውያንን 'እናንተ አንገተ ደንዳና ሕዝብ ናችሁ፤ ለአንዳፍታ እንኳ ከእናንተ ጋር አብሬአችሁ ብሄድ አጠፋችሁ ነበር፤ አሁንም ጌጣጌጦቻችሁን አውልቁ፤ እናንተን ምን ማድረግ እንዳለብኝ እወስናለሁ' ብለህ ንገራቸው" አለው። [6]ስለዚህ እስራኤላውያን በኮሬብ ተራራ ላይ ጌጣጌጦቻቸውን አወለቁ።

## የመገናኛው ድንኳን

[7]ሙሴ "የመገናኛው ድንኳን" ብሎ የጠራውን በመውሰድ፣ ከሰፈሩ ውጭ ራቅ ባለ ቦታ ላይ ይተክለው ነበር። እግዚአብሔርን (ያህዌ) መጠየቅ የሚፈልግ ሁሉ ከሰፈሩ ውጭ ወዳለው ወደ መገናኛው ድንኳን ይሄድ ነበር። [8]ሙሴ ወደ ድንኳኑ በወጣ ጊዜ ሕዝቡ በመነሣት ወደ ድንኳኑ እስኪገባ ድረስ በየድንኳኖቻቸው ደጃፍ ላይ ቆመው ይጠባበቁ ነበር። [9]ሙሴ ወደ ድንኳኑ ገብቶ እግዚአብሔር (ያህዌ) ከሙሴ ጋር እየተነጋገረ ሳለ የደመናው ዐምድ ወርዶ

---

አልበኝነት ይሰፍናል።

32፥26 *የእግዚአብሔር የሆነ ሁሉ ወደ እኔ ይምጣ፤* ኢሱ 24፥15፤ 1ነገ ፤ ማቴ 6፥24 ይመ። *ሌዋውያኑም፤* የሌዊ ዘሮች ምናልባት ከመጀመሪያው እንደ ካህናት ሳይታዩ አይቀርም፤ (ዘፍ 29፥34፤ ዘዳ 18፥6-8)። ሆኖም ከጊዜ በኋላ የሙሴ ወንድም ከሆነው ከአሮን ዘሮች በታች ሳይሆኑ አይቀርም፤ (38፥21፤ ዘኍ 3፥9-10፤ 1ዜና 16፥4-6፡37-42 ይመ)።

32፥27 *ወንድሙን፣ ጓደኛውንና ጎረቤቱን ይግደል፤* ማቴ 10፥37፤ ሉቃ 14፥26 ይመ።

32፥28 *ሌዋውያኑ ሙሴ እንዳዘዛቸው ፈጸሙ፤* ሌዋውያኑ ለእግዚአብሔር ያሳዩት መንፈሳዊ ቅንዓት የአሮን የልጅ ልጅ ፊንሐስ ካሳየው ቅንዓት ጋር የሚመሳሰል ሲሆን ይህም ዘሮቹ ለዘላለም ካህናት እንዲሆኑ አድርጓቸዋል (ዘኍ 25፥7-13)።

32፥29 *በዛሬዋ ቀን... የተለያችሁ ሆናችኋል፤* ሌዋውያኑ ለእግዚአብሔር ካሳዩት መንፈሳዊ ቅንዓት የተነሣ፣ በማደሪያው ድንኳን ውስጥ እንዲያገለግሉትና ካህናቱን እንዲያግዙ ለእግዚአብሔር ተለዩ (ዘኍ 1፥47-53፡3፥5-9፡12፡41፡45፡4፥2-3 ይመ)።

32፥30 *ኀጢአታችሁን ማስተስረይ እችል ይሆናል፤* ሙሴን እግዚአብሔር በራሱና በእስራኤል መካከል ማእከል እንዲሆን የሾመው ሰው በመሆኑ በእግዚአብሔር ፊት ፈጥኖ ኀጢአታቸውን ተናዘዘ። እስራኤላውያንም ሆኑ ሙሴ የሚያቀርቡት መሥዋዕት ይህን ኀጢአት ከቶ ሊያስተሰርይ አይችልም። ሙሴ ግን ራሱን ከሕዝቡ ጋር አንድ ከማድረጉ የተነሣ እግዚአብሔር ሕዝቡን ከማጥፋቱ በፊት እርሱን እንዲያጠፋው ጠየቀ፤ (ቍ 32 ይመ)። ታላቁ ይቅር ባይ ኢየሱስ ክርስቶስ የሕዝቡን ኀጢአት ለማስተስረይ ሲል ራሱን በመስቀል ላይ ሠዋ።

32፥32 *ከጻፍኸው መጽሐፍ፤* የመዝ9፥5፡51፥1፡69፥28 ማብ ይመ።

32፥33 *የበደለኝን ሁሉ... እደመስሰዋለሁ፤* በሕዝቡ ምትክ ለመሞት ራሱን ቢያቀርብም እግዚአብሔር ግን አልተቀበለውም፤ ምክንያቱም ኀጢአትን የሠራ ሰው ለሠራው ኀጢአት ተጠያቂ ነው (ዘዳ 24፥16፤ ሕዝ 18፥4 እና ማብ ይመ)።

32፥34 *አሁን ሂድ፤ ሕዝቡን ... ምራው፤* እግዚአብሔር ከአንገተ ደንዳናዋና ከአመፀኛው እስራኤል ጋር የገባውን ቃል ኪዳን ጠብቆ የተስፋዪቱን ምድር እንደሚሰጥ ለሙሴ አረጋገጠለት። *ወደ ነገርሁህ ስፍራ፤* ከነዓን ማለት ነው (33፥1 ይመ)።

33፥2 *ከነዓናውያንን ... ኢያቡሳውያንን፤* የ3፥8 ማብ ይመ።

33፥3 *ማርና ወተት ወደምታፈሰው ምድር፤* የ3፥8 ማብ ይመ። *ከእናንተ አልሄድም፤* ከዚህ በፊት እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር እንደሚሆን ቢያረጋግጥላቸውም፣ (23፥21 እና ማብ ይመ)፤ አሁን ግን በኀጢአታቸው ምክንያት ለጊዜው ከእነርሱ ጋር እንደማይሆን ተናገረ። *አንገተ ደንዳና፤* የ32፥9 ማብ ይመ።

33፥6 *ጌጣ ጌጦቻቸውን አውልቀው፤* የኀዘን ምልክት ነው (ሕዝ 16፥17 ይመ)።

33፥7 *ከሰፈሩ ውጭ ወዳለው ወደ መገናኛው ድንኳን፤* በእስራኤል ሰፈር መካከል ያለውን የመገናኛ ድንኳን ሳይሆን፣ (ከ27፥21 ጋር ያነጻጽሩ) ቋሚ የሆነው የመገናኛ ድንኳን እስኪታነጽ ድረስ ሕዝቡ ወደ እግዚአብሔር ቀርቦ ጥያቄውን የሚያስቀርብበት ጊዜያዊ ድንኳን ማለት ነው።

33፥9 *የደመናው ዓምድ ወርዶ፤* "ሰው ከወዳጁ ጋር እንደ

በመግቢያው ላይ ይቆም ነበር። [10]ሕዝቡ የደመናውን ዓምድ በድንኳኑ ደጃፍ ላይ ቆሞ ሲያዩት ሁሉም በየድንኳኖቻቸው ደጃፍ ላይ ቆመው ይሰግዱ ነበር። [11]ሰው ከባልንጀራው ጋር እንደሚነጋገር *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከሙሴ ጋር ፊት ለፊት ይነጋገር ነበር፤ ከዚያም ሙሴ ወደ ሰፈሩ ይመለሳል፤ ረዳቱ የነበረው ብላቴናው የነዌ ልጅ ኢያሱ ግን ከድንኳኑ አይለይም ነበር።

### ሙሴና የእግዚአብሔር ክብር

[12]ሙሴ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) አለው፤ "እነዚህን ሕዝብ ምራ' ብለህ ነግረኸኝ ነበር፤ ከእኔ ጋር የምትልከው ማን እንደሆነ ግን አላሳወቅኸኝም፤ 'አንተን በስም አውቅሃለሁ፤ በፊቴም ሞገስ አግኝተሃል' ብለህ ነበር። [13]በእኔ ደስ ተሰኝተህ ከሆነ፣ አንተን ዐውቅህና ያለማቋረጥ በፊትህ ሞገስ አገኝ ዘንድ መንገድህን አስተምረኝ፤ ይህ ሕዝብ የአንተ ሕዝብ መሆኑን አስታውስ።"

[14]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) "ህልዎቴ ከአንተ ጋር ይሄዳል፤ ዕረፍትም እሰጥሃለሁ" ብሎ መለሰ።

[15]ከዚያም ሙሴ እንዲህ አለው፤ "ህልዎትህ ከእኛ ጋር ካልሄደ ከዚህ አትስደደን። [16]አንተ ከእኛ ጋር ካልሄድህ፣ አንተ በእኔና በሕዝብህ መደሰትህን ሌላው እንዴት ያውቃል? እኔንና ሕዝብህንስ በገጸ ምድር ከሚገኙት ከሌሎቹ ሕዝቦች ሁሉ ልዩ የሚያደርገን ሌላ ምን አለ?"

[17]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን፣ "በአንተ ደስ ስላለኝና በስም ስለማውቅህ፣ የጠየቅኸውን ያንኑ አደርጋለሁ" አለው።

[18]ከዚያም ሙሴ "እባክህ፤ ክብርህን አሳየኝ" አለው።

[19]*እግዚአብሔር* (ያህዌ)እንዲህ አለ፤ "መልካምነቴ ሁሉ በፊትህ እንዲያልፍ አደርጋለሁ፤ በፊትህም ስሜን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ዐውጃለሁ፤ ለምምረው ምሕረት አደርጋለሁ፤ ለምራራለትም ርኅራኄ አደርጋለሁ፤ [20]ነገር ግን፣ ማንም እኔን አይቶ መኖር ስለማይችል፣ ፊቴን ማየት አትችልም።"

[21]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዲህ አለ፤ "በአጠገቤ ስፍራ አለ፤ አንተም በዐለት ላይ ትቆማለህ፤ [22]ክብሬ በዚያ ሲያልፍ በዐለቱ ስንጥቅ ውስጥ አደርግሃለሁ፤ በዚያም እስከማልፍ ድረስ በእጄ እጋርድሃለሁ፤ [23]ከዚያም እጄን አነሣለሁ፤ ጀርባዬንም ታያለህ፤ ፊቴ ግን መታየት የለበትም።"

### አዲሶቹ የድንጋይ ጽላቶች

**34** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ "እንደ መጀመሪያዎቹ ያሉ ሁለት የድንጋይ ጽላቶች ጥረብ፤ እኔም አንተ በሰበርካቸው በመጀመሪያዎቹ ጽላቶች ላይ የነበሩትን ቃሎች እጽፍባቸዋለሁ። [2]በማለዳ ተዘጋጅተህ ወደ ሲና ተራራ ውጣ፤ በዚያ በተራራው ጫፍ ላይ በፊቴ ቁም፤ [3]ከአንተ ጋር ማንም እንዳይመጣ ወይም በተራራው ላይ በየትኛውም ቦታ እንዳይታይ፤ የበግና የፍየል መንጋዎች የቀንድ ከብቶችም እንኳ፣ በተራራው ፊት ለፊት መጋጥ የለባቸውም።"

[4]ስለዚህ ሙሴ እንደ መጀመሪያዎቹ ያሉ ሁለት የድንጋይ ጽላቶች ጠርቦ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዳዘዘው በማለዳ ወደ ሲና ተራራ ወጣ፤ ሁለቱን የድንጋይ ጽላቶችም በእጆቹ ያዘ። [5]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በደመና ወረደ፤ በዚያም ከእርሱ ጋር ቆሞ ስሙን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ዐወጀ። [6]እርሱም በሙሴ ፊት እንዲህ ሲል እያወጀ አለፈ፤ "*እግዚአብሔር* *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ርኅሩኅና ቸር አምላክ (ኤሎሂም) ለቍጣ የዘገየ፣

33፥10 ቍ8
33፥11 ዘፀ17፥9፤ ዘኍ12፥8፤ዘዳ5፥4፤ 34፥10
33፥12 ቍ17፤ ዘፍ6፥8፤ዘፀ3፥10፤ 15፥17፤ኢሳ43፥1፤ 45፥3፤49፥1፤ ዮሐ10፥14-15፤ 2ጢሞ2፥19
33፥13 ዘፀ3፥7፤ ዘዳ9፥26፡29፤ መዝ25፥4፤27፥11፤ 51፥13፤77፥15፤ 86፥11፤103፥7፤ 143፥8
33፥14 ዘፀ13፥21፤ ዘዳ4፥37፤12፥9፡10፤ 25፥19፤1ነገ8፥56፤ 2፥4፤ኢያ1፥13፤ 11፥23፤21፥44፤ 22፥4፤23፥1፤ ኢሳ63፥9፡14፤ ኤር31፥2፤ሐጌ1፥13፤ 2፥4፤ማቴ11፥28፤ ዕብ4፥1-11
33፥15 ቍ3፤ ዘፀ34፥9፤2ነገ13፥23፤ 17፥18፤23፥27፤ 24፥20፤መዝ51፥11፤ 80፥3፡7፡19፤ኤር7፥1 5፤52፥3
33፥16 ዘፀ34፥5፡ 10፤ 40፥34፡35፤ዘሌ 20፥24፡26፤ዘኍ9፥15 ፤14፥14፤23፥9፤ዘዳ 4፥7፡32፡34፤32፥9፤ 33፥28
33፥17 ዘፍ6፥8፤ ዘፀ34፥28፤ዘዳ9፥18፡ 25፤10፥10፤ያዕ5፥16
33፥18 ዘፀ16፥7፤ ዮሐ1፥14፤12፥41፤ 1ጢሞ6፥16፤ ራእ15፥8
33፥19 ዘፀ6፥3፤ 34፥5-7፤1ነገ19፥11 ፤ሮሜ9፥15
33፥20 ዘፍ16፥13፤ ዘፀ3፥6፤ዘዳ5፥26፤ ዮሐ1፥18
33፥22 ዘፍ49፥24፤ 1ነገ19፥9፤መዝ27፥5፤ 31፥20፤62፥7፤91፥1፡ 4፤ኢሳ2፥21፤49፥21 51፥16፤ኤር4፥29

34፥1 ዘፀ24፥12፤ 32፥19፤ዘዳ10፥2፡4 34፥2 ዘፀ19፥11
34፥3 ዘፀ19፥13 34፥4 ዘፀ32፥15፤ዘዳ10፥3
34፥5 ዘፀ13፥21፤ 19፥9፤6፥3፤33፥19 34፥6 ዘፍ19፥16፤ ዘፀ22፥27፤ ዘኍ14፥18፡20፤መዝ61፥7፤78፥38፤86፥15፤108፥4፤ 115፥1፤ 138፥2፤143፥1፤ኤር 15፥15፤ሰቆ3፥23፤ ሮሜ2፥4፤ያዕ5፥11

ሚነጋገር" (ቍ 11) እግዚአብሔር ከሙሴ ጋር የሚያደርገውን ግንኙነት ያመለክታል። የማደሪያው ድንኳን ተሠርቶ ከተጠናቀቀ በኋላም ድንኳኑ በደመና ተሸፍኖ ነበር፤ (40፡33-34፤ የ13፥21 ማብ ይመ)።

33፥11 *እግዚአብሔር ከሙሴ ጋር ፊት ለፊት ይነጋገር ነበር፤* ሙሴ የብሉይ ኪዳን መካከለኛ በመሆኑ ከነቢያት ሁሉ የተለየ ነበር። *ኢያሱ ግን ከድንኳኑ አይለይም ነበር፤* የኢያሱ ሥራ፣ ሰዎች ወደ ድንኳኑ ዘው ብለው እንዳይገቡ ምናልባት መጠበቅ ሊሆን ይችላል።

33፥12 *ከእኔ ጋር የምትልከው ማን እንደ ሆነ ግን አላሳወቅኸኝም፤* የቍ 3 ማብ ይመ። ሙሴ በዚህ ቦታ የሚናገረው ማንኛውም መልአክ የእግዚአብሔርን መገኘት እንደማይተካ ነው። *አንተን በስም አውቅሃለሁ፤* እንዲህ ሲለው ለተለየ ተልዕኮ ዬ መርጬሃለሁ ማለቱ ነው።

33፥13 *መንገድህን አስተምረኝ፤* በ34፥6-7 ላይ የተመለሰ ጸሎት ነው።

33፥14 *ህልዎቴ ካንተ ጋር ይሄዳል፤* ሙሴ ለተጨነቀበት ጕዳይ (የቍ12 ማብ ይመ) እግዚአብሔር የሰጠው ቸርነት የተሞላ መልስ ነው፤ የእኔ መገኘት ካንተ ጋር ይሆናል ማለቱ ነው።

33፥17 *በአንተ ደስ ስላለኝ፤* እግዚአብሔር የልጁን የኢየሱስ ክርስቶስን ጸሎት እንዴት አብልጦ ይሰማ ይሆን! (ማቴ 17፥5፤ ዕብ 3፥1-6 ይመ)

*33፥18፤* ቍ 22 ይመ። ይህ የሙሴ ጸሎት የኢየሱስ መልክ በተለወጠበት ተራራ ላይ፣ የኢየሱስን ክብር ለአጭር ጊዜ ከኤልያስና ከኢየሱስ ሦስት ደቀመዛሙርት ጋር ባየ ጊዜ ተመልሶአል ማለት ይቻላል፤ (ሉቃ 9፥30-32)።

33፥19 *መልካምነቴ፤* የእግዚአብሔርን ባሕርይና ጠባይ ያሳያል። *ስሜን፤* የእግዚአብሔርን ባሕርይ ጠባይና ማንነት የበለጠ የሚያመለክት ነው፤ (መዝ 20-1፡ዮሐ 1፥12፡17፥6 ይመ)። ስሙ በዚህ ስፍራ ምሕረቱንና (ጸጋውን) ርኅራኄውን (በ34፥6 ላይ እንደ ተጠቀሰው) ያሳይል።

*33፥20፤* የዘፍ 16፥13 ማብ፤ ዮሐ 1፥18፡6፥46፤ 1ጢሞ 1፥17፤ 1ዮሐ 4፥12 ይመ።

*33፥21-23፤* እግዚአብሔር ስለ ራሱ በሰው ቋንቋ ይናገራል። በዚህ ቦታ ለሙሴ የገባለትን ቃል በ34፥5-7 ላይ ፈጽሞለታል።

34፥1 *ሁለት የድንጋይ ጽላቶች ... እጽፍባቸዋለሁ፤* የ31፥18 ማብ ይመ። *ቃላት፤* የ20፥1 ማብ ይመ።

34፥5 *ስሙን፤* የ33፥19 ማብ ይመ።

*34፥6-7፤* 33፥19 እና ማብ ይመ። እግዚአብሔር በእነዚህ ቍጥሮች ላይ ስለ ራሱ ስም የሰጠው ትርጓሜና ማብራሪያ በሌሎች የብሉይ ኪዳን ክፍሎች ላይ ተዘውትሮ ተወስቶአል፤ (ዘኍ 14፥18፤ ነህ 9፥17፤ መዝ 86፥15፡ 103፥8፤ 145፥8፤ ኢዩ 2፥13፤

ፍቅሩና ታማኝነቱ የበዛ፣ [7]ፍቅርን ለሺዎች የሚጠብቅ፣ ክፋትን፣ ዐመፅንና ኀጢአትን ይቅር የሚል፣ በደለኛውን ግን ሳይቀጣ ዝም ብሎ አይተውም፤ በአባቶች ኀጢአት ልጆችን የልጅ ልጆቻቸውን እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ይቀጣል።"

[8]ሙሴም ወዲያውኑ ወደ መሬት ዝቅ ብሎ ሰገደ፤ [9]"አቤቱ ጌታ (አዶናይ) ሆይ፤ በፊትህ ሞገስ አግኝቼ ከሆነ፣ ጌታ (አዶናይ) ከእኛ ጋር ይሂድ፤ ይህ አንገተ ደንዳና ሕዝብ ቢሆንም እንኳ፣ ክፋታችንንና ኀጢአታችንን ይቅር በል፤ እንደ ርስትህም አድርገህ ውሰደን።"

[10]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲህ አለ፤ "ከአንተ ጋር ቃል ኪዳን አደርጋለሁ፤ ከዚህ ቀደም በዓለም ሁሉ ለየትኛውም ሕዝብ ከቶ ያልተደረገ፣ በሕዝብህ ሁሉ ፊት ድንቅ አደርጋለሁ፤ በመካከላቸው አብረሃቸው የምትኖር ሕዝብ እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) ለአንተ የማደርግልህ ሥራ የቱን ያህል አስፈሪ እንደ ሆነ ያያሉ። [11]ዛሬ የማዝህን ፈጽም፤ አሞራውያንን፣ ከነዓናውያንን፣ ኬጢያውያንን፣ ፌርዛውያንን፣ ኤዊያውያንንና ኢያቡሳውያንን በፊትህ አስወጣቸዋለሁ። [12]ከምትሄድበት አገር ነዋሪዎች ጋር ቃል ኪዳን እንዳታደርግ ተጠንቀቅ፤ አለዚያ በመካከልህ ወጥመድ ይሆኑብሃል። [13]መሠዊያዎቻቸውን ሰባብሩ፤ የማምለኪያ ዐምዶቻቸውን አድቅቁ[ז]፤ የአሼራ ዐፀዶቻቸውንም ቍረጡ። [14]ስሙ ቀናተኛ የሆነው እግዚአብሔር (ያህዌ) ቀናተኛ ስምላክ (ኤል) ነውና ሌላ አምላክ አታምልክ።

[15]"በምድሪቱ ከሚኖሩት ጋር ቃል ኪዳን እንዳታደርግ ተጠንቀቅ፤ ምክንያቱም አምላኮቻቸውን ተከትለው ባመነዘሩና መሥዋዕትም ባቀረቡላቸው ጊዜ ይጋብዙሃል፤ አንተም መሥዋዕታቸውን ትበላለህ። [16]ለወንዶች ልጆችህም ሴቶች ልጆቻቸውን ስታጭላቸውና እነዚህም ሴቶች ልጆች አምላኮቻቸውን በመከተል ሲያመነዝሩ፣ ወንዶች ልጆችህን ተመሳሳይ ድርጊት እንዲፈጽሙ ያነሣሡአቸዋል።

[17]"ቀልጠው የሚሠሩ አማልክትን አታብጅ።

[18]"የቂጣን በዓል አክብር። እንዳዘዝኩህም ለሰባት ቀን እርሾ ያልገባበት ቂጣ ብላ፤ ይህንንም በተወሰነው ጊዜ በአቢብ ወር አድርግ፤ በዚያ ወር ከግብፅ ወጥተሃልና።

[19]"የመንጋህ ወይም የበግና የፍየልህ፣ የቀንድ ከብትህ ተባዕት በኵር ሁሉ ሳይቀር፣ ከማሕፀን በኵር ሆኖ የሚወጣ ሁሉ የእኔ ነው። [20]የአህያን በኵር በበግ ጠቦት ዋጀው፤ ካልዋጀኸው ግን አንገቱን ስበረው። በኵር ወንድ ልጆችህን ሁሉ ዋጅ።

"ማንም በፊቴ ባዶ እጁን አይቅረብ።

[21]"ስድስት ቀን ሥራ፤ በሰባተኛው ቀን ግን ዕረፍ፤ በዕርሻና በመከር ወቅት እንኳ ቢሆን ማረፍ አለብህ።

[22]"የሰባቱን ሱባዔ በዓል ከስንዴው መከር በኵራቶች ጋር፣ እንዲሁም የመክተቻ በዓልን በዓመቱ መጨረሻ[ሠ] ላይ አክብር። [23]በዓመት ሦስት ጊዜ ወንድ ሁሉ በእስራኤል ስምላክ (ኤሎሂም) በልዑል እግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ይቅረብ። [24]አሕዛብን ከፊትህ አስወጣለሁ፤ ድንበርህን አሰፋለሁ፤ በዓመት ሦስት ጊዜ በአምላክህ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ለመቅረብ ስትወጣ፣ ምድርህን ማንም አይመኝም።

[25]"እርሾ ካለው ከማንኛውም ነገር ጋር የደም መሥዋዕት ለእኔ አታቅርብ፤ ከፋሲካ በዓል የተረፈው መሥዋዕት እስከ ማለዳ አይቆይ።

[26]"የአፈርህን ምርጥ በኵራት ለአምላክህ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ቤት አምጣ።

"ጠቦት ፍየልን በእናቱ ወተት አትቀቅል።"

[27]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "እነዚህን ቃሎች ጻፋቸው፤ በእነዚህ ቃሎች መሠረት ከአንተና ከእስራኤል ጋር ቃል

34፥7 ዘፀ20፥5፡6፤ 23፥7፤ዘዳ5፥10፤1ነገ 8፥30፤ኢሱ24፥19፤ ኢዮ7፥20-21፤9፥28፤ 10፥14፤መዝ86፥5፤ 103፥3፤130፥4፡8፤ ኢሳ43፥25፤ዳን9፥9፤ ሚክ6፥1-16፤ ናሆ1፥3፤1ዮሐ1፥9
34፥9 ዘፀ6፥7፤ 19፥5፤32፥9፤33፥13፡ 15፤ዘኍ6፥7፤11፥15፤ 14፥19፤19፥5፤ዘዳ4፥ 20፤7፥6፤9፥26፡29፤ 14፥2፤26፥18፤32፥9፤ 1ነገ8፥30፡51፡53፤ 1ሳሙ10፥1፤2ሳሙ 14፥16፤2ዜና6፥21፤ መዝ19፥12፤25፥11፤ 28፥9፤33፥12፤74፥2፤ 79፥1፤94፥14፤106፥5 ፡40፤ኢሳ19፥25፤ 63፥17፤ኤር10፥16፤ 33፥8፤51፥19፤ ሆሴ 14፥2፤ ሚክ7፥18፤ ዘካ2፥12
34፥10 ዘፍ6፥18፤ 9፥15፤15፥18፤ዘፀ 3፥20፤33፥16፤ዘዳ 5፥2-3
34፥11 ዘፀ23፥28፤ ዘዳ6፥25፤ኢሱ11፥15
34፥12 ዘፀ10፥7፤ መሳ2፥2
34፥13 ዘፀ23፥24፤ ዘኍ33፥52፤ዘዳ7፥5፤ 12፥3፤መሳ6፥26፤1ነገ 15፥13፤2ዜና15፥16፤ 17፥6፤34፥3-4፤ሚክ 5፥14
34፥14 ዘፀ20፥3፡5፤ ኢሳ9፥6
34፥15 ቍ12፤ዘፀ 22፥20፤32፥6፡8፤ዘዳ 23፥6፤31፥16፤መሳ 2፥17፤2ነገ17፥8፤ 1ዜና5፥25፤2ዜና 11፥15፤ዕዝ9፥12፤ አሞ2፥4፤1ቆሮ8፥4
34፥16 ዘዳ7፥3፡4፤ 12፥31፤17፥17፤ 20፥18፤ኢሱ23፥12፤ መሳ3፥6፤ 14፥3፤1ነገ11፥1፡2፡4፤ 16፥31፤2ነገ21፥3- 15፤ዕዝ9፥2፤10፥3፤ ነህ10፥30፤ 13፥25፡26፤ መዝ106፥34-41፤ ሚል2፥11
34፥17 ዘፀ20፥4
34፥18 ዘፀ12፥2፡15፡17፤ቱ26፥17፤ሉቃ22፥1፤ሐሥ12፥3
34፥19 ዘፀ13፥2 34፥20 ዘፀ13፥2፡13፤22፥29፤ ዘዳ16፥16፤ ሕዝ 46፥9 34፥21 ዘፍ2፥2-3፤ነህ13፥15፤ኢሳ56፥2፤58፥13
34፥22 ቍ26፤ዘፀ23፥16፡19፤ዘሌ2፥12፡14፤7፥13፤23፥10፡17፤ ዘኍ28፥26 34፥23 ዘፀ23፥14 34፥24 ዘፀ23፥28፤ ዘዳ12፥20፤19፥8፤ ኢዮ12፥23 34፥25 ዘፀ12፥8፤ 23፥18፤
34፥26 ዘፀ22፥29፤ 23፥19፤ዘኍ18፥12 34፥27 ዘፍ6፥18፤ 15፥18፤ዘፀ17፥14

[ז]13 አሼራ የምትባለውን ጣዖት አምላክ ምስል ማለት ነው።
[ሠ]22 መስከረም፣ ጥቅምትና ኅዳር ማለት ነው።

ዮና 4፥2 ይመ የ3፥14-15፡6፡2-3 ማብ ይመ)።

34፥7 *ሺህ፤* ወይም "አንድ ሺህ ትውልድ" ማለት ነው፤ (20፥6 ይመ)፤ *ክፋትን ዓመፅንና ኀጢአትን፤* ኢሳ 59፥12 እና ማብ ይመ።

34፥10 *ኪዳን እገባለሁ፤* ቀደም ሲል የገባውን ኪዳን እንደ ገና ሲያጸና ነው፤ (ምዕራፍ 19፥24 ይመ)። ቍ 10-26 እኩል በሆኑ ዐሥር ክፍሎች ሊከፈሉ ስለሚችሉ አንዳንድ ጊዜ ዐሥሩ ቃሚ ትእዛዛት ተብለው ይጠራሉ፤ (ለአብነት ያህል ከቍ 15-26 ያሉት አንቀጾች ይመ)፤ ከቍ 10-26 ያለው ክፍል ቀደም ካሉት የዘፀአት ምዕራፎች ላይ ቃል በቃል የተጠቀሰ ነው (ቍ 18-26 ከ 23፥14-19 ጋር ያነጻጽሩ)።

34፥12 *ከምትሄዱበት አገር ነዋሪዎች ጋር ቃል ኪዳን እንዳታደርግ፤* እስራኤል ከከነዓን ሕዝቦች ምንም ዐይነት የሰላም ውል መዋዋልና እግዚአብሔርም በሚያወርሳት ምድር እንዲኖሩ መፍቀድ የለባትም።

34፥13 *የአሼራ ምሰሶዎቻቸውን፤* አሼራ የከነዓናውያን ዋነኛ አምላክ የኤል ሚስት ስም ነው፤ ምናልባት በእርስዋ ምስል የሚቀረጹ የእንጨት ምሰሶዎች ለእርሷ ክብር ሲባል ከሌሎች የጣዖት አምልኮ ምስሎች ጎን ሳይከተሉ አይቀርም (መሳ 6፥25 ይመ)።

34፥14 *ስሙ 'ቀናተኛ' የሆነው፤* የ20፥5 ማብ ይመ።

34፥15 *ባመነዘሩ ... ጊዜ፤* መሳ 2፥17 እና ማብ ይመ። *መሥዋዕታቸውን ትበላለህ፤* ለጣዖት የተሠዋን ምግብ ከጣዖት አምላኪዎች ጋር መብላት ፈተናን፣ በመጨረሻም አብሮ መተባበርን ያስከትላል፤ (ከ1ቆሮ 8፡10፥18-21 ያነጻጽሩ)።

34፥17 *ቀልጠው የሚሠሩ አማልክትን አታብጅ፤* አሮን የወርቅ ጥጃ እንደሠራ እናንተም አትሥሩ ማለት ነው፤ (32፥4 ይመ)።

*34፥18-26፤* የ23፥14-19 ያለውን ማብ ይመ።

34፥21 *በዕርሻና በመከር ወቅት እንኳ ቢሆን ማረፍ አለብህ፤* የማደሪያውን ድንኳን በሚሠሩበት ጊዜ እንደሚያርፉ ሁሉ፣ አሁንም ማረፍ አለባቸው፤ (የ31፥13፤ 16-17 ማብ ይመ)።

34፥27 *እነዚህን ቃሎች ጻፋቸው፤* ቀደም ብሎ እነዚህኑ ቃላት እንደ ጻፋቸው ሁሉ ማለት ነው፤ (24፥4 ይመ)።

ኪዳን አድርጌአለሁና" አለው:: [28]ሙሴ እህል ሳይበላ ውሃም ሳይጠጣ *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ጋር አርባ ቀንና አርባ ሌሊት በዚያ ነበር፤ በጽላቶቹ ላይ የቃል ኪዳኑን ቃሎች፣ ዐሥርቱ ትእዛዛትን ጻፈ::

### የሚያበራው የሙሴ ፊት

[29]ሙሴ ሁለቱን የምስክር ጽላቶች በእጆቹ ይዞ ከሲና ተራራ በወረደ ጊዜ *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ጋር ከመነጋገሩ የተነሣ ፊቱ እንደሚያበራ አላወቀም ነበር:: [30]አሮንና እስራኤላውያን ሁሉ ሙሴን ባዩት ጊዜ ፊቱ ያበራ ነበር፤ ወደ እርሱ ለመቅረብም ፈርተው ነበር:: [31]ሙሴ ግን ጠራቸው፤ ስለዚህ አሮንና የማኅበሩ መሪዎች ወደ እርሱ ተመለሱ፤ እርሱም አናገራቸው:: [32]ከዚያም በኋላ እስራኤላውያን ሁሉ ወደ እርሱ ቀረቡ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሲና ተራራ የሰጠውን ትእዛዞች ሁሉ ሰጣቸው::

[33]ሙሴ ለእነርሱ ተናግሮ ከጨረሰ በኋላ በፊቱ ላይ መሸፈኛ አደረገ:: [34]ከእርሱ ጋር ለመነጋገር ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ህልዎት በሚገባበት ጊዜ ሁሉ ግን፣ እስከሚወጣ ድረስ መሸፈኛውን ያነሣ ነበር፤ በወጣም ጊዜ የታዘዘውን ለእስራኤላውያን ነገራቸው:: [35]ፊቱ የሚያበራ መሆኑን አዩ፤ ከዚያም ሙሴ *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ጋር ለመነጋገር ተመልሶ እስኪሄድ ድረስ መሸፈኛውን መልሶ በፊቱ ላይ ያደርግ ነበር::

### የሰንበት ሥርዐቶች

**35** ሙሴ የእስራኤልን ማኅበረሰብ ሁሉ ሰብስቦ እንዲህ አላቸው፤ "*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንድትፈጽሟቸው ያዘዛችሁ ነገሮች እነዚህ ናቸው፤ [2]ስድስት ቀን ሥራ ይሠራል፤ ሰባተኛው ቀን ግን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የሰንበት ዕረፍት፣ የተቀደሰ ቀን ይሆንላችኋል፤ በዕለቱ ማናቸውንም ዐይነት ሥራ የሚሠራ ቢኖር ሞት ይገባዋል:: [3]በሰንበት ቀን በማናቸውም መኖሪያዎቻችሁ ውስጥ እሳት አታንድዱ::"

### ለመገናኛው ድንኳን ዕቃዎች

35፥4-9 ተን ምብ - ዘፀ 25፥1-7
35፥10-19 ተን ምብ - ዘፀ 39፥32- 41

[4]ሙሴ ለእስራኤላውያን ማኅበረሰብ ሁሉ እንዲህ አላቸው፤ "*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ያዘዘው ይህ ነው፤ [5]ካላችሁ ንብረት ሁሉ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) መሥዋዕት አቅርቡ፤ ፈቃደኛ የሆነ ማንም *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የወርቅ፣ የብር፣ የናስ መባ ያምጣ፣ [6]ሰማያዊ፣ ሐምራዊና ቀይ ማግ፤ ቀጭን ሐር፣ የፍየል ጠጕር፣ [7]ቀይ የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ፣ እንዲሁም አቆስጣ ቆዳ[a7]፣ የግራር እንጨት፤ [8]ለመብራት የወይራ ዘይት፣ ለቅብዐ ዘይቱና ለጣፋጭ ሽታ ዕጣን ቅመም፤ [9]በኤፉዱና በደረት ኪሱ ላይ የሚሆኑ መረግዶችና ሌሎች ዕንቍዎችን መባ አድርጎ ያምጣ::

[10]"በመካከላችሁ ጥበበኞች የሆኑ ሁሉ መጥተው *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ያዘዘውን ሁሉ ይሥሩ፤ [11]የመገናኛውን ድንኳን ከነድንኳኑና ከነመደረቢያው፣ ማያያዣዎችን፣ ክፈፎችን፣ አግዳሚዎችን፣ ቋሚዎችንና መሠረቶችን፤ [12]ታቦቱን ከነመሎጊያዎቹ፣ የስርየት መክደኛውንና የሚሸፍነውን መጋረጃ፤ [13]ጠረጴዛውን ከነመሎጊያዎቹ፣ ዕቃዎቹን ሁሉና የህልዎቱን ኅብስት፤ [14]ለመብራት የሆነውን መቅረዝ ከነዕቃዎቹ፣ ቀንዲሎችንና ለመብራት የሚሆነውን ዘይት፤ [15]የዕጣን መሠዊያውን ከነመሎጊያዎቹ፣ ቅብዐ ዘይቱንና ጣፋጭ ሽታ ያለውን ዕጣን፤ በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ የሚሆነውን የመግቢያ መጋረጃ፤ [16]የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያውን ከናስ መጫሪያው፣ መሎጊያዎቹንና ዕቃዎቹን ሁሉ፣ የናስ ሰኑን ከነማስቀመጫው፣ [17]ያደባባዩን መጋረጃዎች ከነምሰሶዎቻቸውና ከነመሠረቶቹ፣ ያደባባዩን መግቢያ መጋረጃ፤ [18]ለመገናኛው ድንኳንና ለአደባባዩ የሚሆኑ የድንኳን ካስማዎችና ገመዶቻቸው፤ [19]በመቅደሱ ውስጥ ለማገልገል የሚለበሱ የፈትል ልብሶችን ይኸውም የካህኑ የአሮንን የተቀደሱ ልብሶችንና ካህናት ሆነው ሲያገለግሉ የሚለብሷቸውን የወንዶች ልጆቹን ልብሶች ይሥሩ::"

[20]ከዚያም የእስራኤል ማኅበረሰብ ሁሉ ከሙሴ ፊት ወጡ፤ [21]ፈቃደኛ የነበረና ልቡን ያነሣሣው ሁሉ በመምጣት ለመገናኛው ድንኳን ሥራ፣ ለአገልግሎቱ ሁሉና ለተቀደሱ ልብሶች የሚሆን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) መባ አመጡ:: [22]ፈቃደኛ የነበሩ ሁሉ፣ ወንዶችም ሴቶችም መጥተው ከሁሉም ዐይ

[a7] በዚህና በቍጥር 23 ላይ አንዳንድ ቅጂዎች፣ *የለፋ የአቆስጣ ቆዳ* ይላሉ::

34፥28 ቍ 1፤ ዘኍ7፥4፤ዘፀ31፥18፤ ዘዳ4፥13፤9፥9:18፤ 10፥4፤፤ዕዝ10፥6፤ ማቴ4፥2፤ሉቃ4፥2
34፥29 ቍ35፤ ዘፀ19፥11፤32፥15፤ መዝ34፥5፤ኢሳ60፥5፤ ማቴ17፥2፤2ቆሮ3፥7:13
34፥31 ዘፀ16፥22
34፥32 ዘፀ21፥1፤ 35፥1:4
34፥33 2ቆሮ3፥13
34፥35 ቍ29
35፥1 ዘፀ34፥32
35፥2 ዘኍ2፥3፤ ዘፀ31፥14፤34፥21፤ ዘዳ5፥13-14
35፥3 ዘፀ16፥23
35፥8 ዘፀ25፥6
35፥10 ዘፀ31፥6፤ 39፥43
35፥11 ዘፀ26፥1-37 ፤36፥8-38
35፥12 ዘፀ25፥10-22፤26፥33፤37፥1-9
35፥13 ዘፀ25፥23-30፤37፥10-16
35፥14 ዘፀ25፥31
35፥15 ዘፀ30፥1-6 ፤37፥25-28፤30፥25: 34-38፤26፥36
35፥16 ዘፀ27፥1-8፤30፥18፤38፥1-7
35፥17 ዘፀ27፥9፤ 38፥9-20
35፥18 ዘፀ27፥19፤ 38፥20
35፥19 ዘፀ28፥2

34፥28 *ጻፈ፤* በዚህ ቦታ የዚህ ቃል ባለቤት ሙሴ ሳይሆን እግዚአብሔር ነው፤ (ቍ 1 ይመ)::

34፥29 *የምስክር፤* የ16፥34:25፥16 ማብ ይመ:: *ያበራ፤* የእግዚአብሔርን ክብር ለማየት ሲለምን የነበረው፣ (33፥18) አሁን ሳያስተውለው መለኮታዊውን ክብር አንጸባረቀ::

34፥33 *በፊቱ ላይ መሸፈኛ፤* እንዲህ ያደረገው እስራኤላውያን እየቀነሰ የሚመጣውን ነጸብራቅ እንዳያዩና እግዚአብሔርን ወክሎ በፊታቸው የሚያገለግለውን ሙሴን ማክበራቸውን እንዲቀጥሉ ለማድረግ ነው፤ (2ቆሮ 3፥7-18 እና ማብ ይመ)::

*35፥1-31* እስራኤላውያን የመገናኛውን ድንኳንና የካህናቱን ልብስ እንዴት መሥራት እንዳለባቸው መመሪያ ከተሰጣቸው በኋላ ሰንበትን መጠበቅ እንዳለባቸው ማሳሰቢያ እንደተሰጣቸው ሁሉ፣ (የ31፥13 ማብ ይመ) አሁንም እነዚያን መመሪያዎች ከመፈጸማቸው በፊት ተመሳሳይ ማሳሰቢያ ለሕዝቡ ተሰጥቶአል::

*35፥4-39፥43፤* ይህ ክፍል አብዛኛውን የተወሰደው ከም 25-28፤ 30፥1-5፤31፥1-11 ነው፤ (የእነዚህን ክፍሎች ማብ ይመ)፤ አንዳንድ ጊዜ ቃል በቃል፣ ሌላ ጊዜ ደግሞ ግሦቹ በትንቢት ጊዜ መጠቀስ ሲገባቸው፣ በኃላፊ ጊዜ ተጠቅሰውና አርእስቱም በተለየ ቅደም ተከተል ተስተካክለው እናገኛቸዋለን:: እንዲህ ያለውን ድግግሞሽ በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ ሥነ ጽሑፎች ውስጥ ማየት የተለመደ ሲሆን፣ እንዲህ የሚደረገውም ዝርዝር ታሪኩን በተደራሲዎች ኅሊና ውስጥ አትሞ ለማስቀረት ነው፤ (የዘፍ 24፥34-49 ማብ ይመ)::

35፥5 *ፈቃደኛ የሆነ፤* በራስ ፈቃደኝነት ተነሣሥቶ የቍሳቍስም ሆነ የጒልበት መሥዋዕት ማቅረብ አስፈላጊ መሆኑን አበክሮ የሚያስገነዝብ ነው፤ (ቍ 21-22:26:29፤ 36፥2-3 ይመ)::

35፥21 *ለመገናኛው ድንኳን፤* የ27፥21 ማብ ይመ::

ነት የወርቅ ጌጦች አመጡ፤ የአፍንጫ ጌጠ ችን፣ ሎቲዎችን፣ ቀለበቶችን፣ ድሪዎችንና ጌጣ ጌጦችን ሁሉ አመጡ፤ ሁሉም ወርቃ ቸውን እንደሚወዘውዝ መሥዋዕት ለእግዚ አብሔር (ያሕዌ) አቀረቡ። [23]ሰማያዊ፣ ሐምራዊ ወይም ቀይ ማግ ወይም ቀጭን ሐር ወይም የፍየል ጠጕር፣ ቀይ የተነከረ የአውራ በግ ቆዳ ወይም የአቆስጣ ቆዳ አመጡ። [24]የብር ወይም የናስ መባ ማቅረብ የቻሉ ሁሉ ለእግዚአብሔር (ያሕዌ) መባ አድርገው አመጡ፤ የግራር ዕንጨት ያለው ሁሉ አስፈላጊ በሆነው ሥራ እንዲውል አመጣው። [25]ጥበበኞች የሆኑ ሴቶች ሁሉ በእጃቸው ፈትሉ የፈ ተሉትንም ሰማያዊ ሐምራዊ ወይም ቀይ ማግ ወይም ቀጭን በፍታ አመጡ። [26]ፈቃ ደኛ የነበሩና ጥበቡ ያላቸው ሴቶች ሁሉ የፍየል ጠጕር ፈተሉ። [27]መሪዎቹም ኤፉ ድና በደረት ኪሱ ላይ እንዲሆን የከበሩ ድንጋዮችንና ሌሎች ዕንቍዎች አመጡ። [28]እንዲሁም ለመብራቱ፣ ለቅብዐ ዘይቱና ለጣፋጭ ሽታ ዕጣን የሚሆኑ ቅመሞችንና የወይራ ዘይትን አመጡ። [29]ፈቃደኛ የሆኑ እስራኤላውያን ወንዶችና ሴቶች ሁሉ፣ እግዚአብሔር (ያሕዌ) በሙሴ በኩል እንዲያከ ናውኑት ላዘዛቸው ሥራ ሁሉ የበጎ ፈቃድ ስጦታዎችን ለእግዚአብሔር (ያሕዌ) አመጡ።

## ባስልኤልና ኤልያብ

35፥30-35 ተጓ ምብ - ዘፀ 31፥2-6

[30]ከዚያም ሙሴ እስራኤላውያንን አላቸው፤ “እነሆ፣ እግዚአብሔር (ያሕዌ) ከይሁዳ ነገድ የሆነውን የሆር ልጅ፣ የኡሪን ልጅ ባስልኤ ልን መርጦአል። [31]በጥበብ፣ በችሎታና በዕ ውቀት፣ በማናቸውም ዐይነት ሙያ የእግዚ አብሔርን (ኤሎሂም) መንፈስ ሞልቶበታል፤ [32]ይኸ ውም በወርቅ፣ በብርና በናስ የጥበብ ሥራ እንዲሠራ ነው፤ [33]ድንጋዮችን እንዲጠርብና እንዲያወጣ፣ የዕንጨት ሥራ እንዲሠራና ማንኛውንም ዐይነት የጥበብ ሙያ እንዲያ ከናውን ነው። [34]እንዲሁም ለእርሱና ከዳን ነገድ ለሆነው ለአሂሳሚክ ልጅ ለኤልያብ፣ ለሁለቱም ሌሎችን የማስተማር ችሎታ ሰጣቸው። [35]የጥበብ ባለሙያዎች፣ ዕቅድ አውጭዎች፣ በሰማያዊ በሐምራዊና በቀይ ማግ፣ በቀጭን ሐር ጥልፍ ጠላፊዎችና ፈታ ዮች፤ ሁሉም ዋና የጥበብ ባለሙያዎችና ዕቅድ አውጭዎች በመሆን ማንኛውንም ዐይነት ሥራ ያከናውኑ ዘንድ በጥበብ ሞልቶአቸዋል።

36 ስለዚህ የመቅደሱን የማንባታ ሥራ ሁሉ እንዴት ማከናወን እንዳለባ ቸው እግዚአብሔር (ያሕዌ) ጥበብንና ችሎታን የሰጣቸው፣ ባስልኤል፣ ኤልያብና ጥበበኛ የሆኑ ሰዎች ሁሉ ሥራውን ልክ እግዚአ ብሔር (ያሕዌ) እንዳዘዘው ይሥሩት።”

[2]ከዚያም ሙሴ ባስልኤልንና ኤልያብን እንዲሁም እግዚአብሔር (ያሕዌ) ችሎታ የሰጣ ቸውን፣ መጥተው ሥራውን ለመሥራት ፈቃደኛ የሆኑትን ጥበብ ያላቸውን ሰዎች ሁሉ አስጠራ። [3]የመቅደሱን የማንባታ ሥራ ለማከናወን እስራኤላውያን ያመጡትን ስጦታ ሁሉ ከሙሴ ተቀበሉ፤ ሕዝቡ የበጎ ፈቃድ ስጦታዎችን በየማለዳው ማምጣታቸውን ቀጠሉ። [4]ስለዚህ የመቅደሱን ሥራ ሁሉ ይሠሩ የነበሩ ጥበበኞች የሆኑ ባለሙያዎች ሁሉ ሥራቸውን ትተው መጡ፤ [5]ሙሴንም፣ “ሕዝቡ እግዚአብሔር (ያሕዌ) እንዲሠራ ላዘዘው ሥራ ከበቂ በላይ እያመጡ ነው” አሉት። [6]ከዚ ያም ሙሴ ትእዛዝ ሰጠ፤ ይህንንም ቃል ወደ ሰፈሩ ላኩት፤ “ማንም ወንድ ወይም ሴት ለመቅደሱ ሌላ ምንም ስጦታ ማድረግ የለበ ትም፤” ስለዚህ ሕዝቡ ትርፍ እንዳያመጡ ተከለከሉ፤ [7]ምክንያቱም ሥራውን ሁሉ ለማ ከናወን በእጃቸው ያለው ከበቂ በላይ ነበረ።

## የማደሪያው ድንኳን

36፥8-38 ተጓ ምብ - ዘፀ 26፥1-37

[8]የሥራ ችሎታ ካላቸው ሰዎች መካከል ጥበበኛ የሆኑ ሰዎች ሁሉ የማደሪያውን ድንኳን በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ ከሰማ ያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ፣ በጥልፍ ዐዋቂ ኪሩቤል ከተጠለፉበት ከዐሥር መጋ ረጃዎች ሠሩት። [9]መጋረጃዎቹም ሁሉ ተመሳሳይ መጠን ያላቸው ሲሆን፣ ቁመ ታቸው ሃያ ስምንት ክንድ፣ ወርዳቸው አራት ክንድ[a] ነበር። [10]አምስቱን መጋረጃ ዎች ባንድ ላይ በማጋጠም ሰፉቸው፤ የቀሩ ትን አምስቱንም እንዲሁ አደረጉ። [11]ተጋ ጥሞ ከተሰፋው መጋረጃ ጠርዝ ጫፍ ላይ ከሰማያዊ ግምጃ ቀለበቶችን አበጁ፤ ተጋጥሞ በተሰፋው በሌላው መጋረጃ ጫፍ ላይም ተመሳሳይ ነገር አደረጉ። [12]በአንደኛው መጋረጃ ላይ አምሳ ቀለበቶችን በሌላው ተጋጥሞ ከተሰፋው በስተ መጨረሻ ካለው መጋረጃ ላይ አምሳ ቀለበቶችን እርስ በርሳ ቸው ትይዩ በማድረግ ሠሩት። [13]ከዚያም አምሳ የወርቅ ማያያዣዎችን ሠሩ፤ የማደሪ ያው ድንኳን አንድ ወጥ ይሆን ዘንድም ተጋጥመው የተሰፉትን ሁለቱን መጋረጃዎች አያያዙባቸው።

[14]ከማደሪያው በላይ ለሚሆነው ድንኳን ከፍየል ቆዳ የተሠሩ በጠቅላላ ዐሥራ አንድ መጋረጃዎችን ሠሩ። [15]ዐሥራ አንዱ መጋ ረጃዎች ተመሳሳይ ልክ ሲኖራቸው፣ ቁመ ታቸው ሠላሳ ክንድ፣ ወርዳቸውም አራት ክንድ[a] ነበር። [16]አምስቱን መጋረጃዎች በአ ንድ በኩል፣ ሌሎቹን ስድስት መጋረጃ ዎች ደግሞ በሌላ በኩል አንድ ላይ አያያ ዟቸው። [17]በስተመጨረሻ በሚገኘው መጋ ረጃ ጠርዝ ላይ አምሳ ቀለበቶችን፣ በሌላ በኩል ባለው በስተ መጨረሻ በሚገኘው

35፥23 ዘፀ39፥1
35፥25 ዘፀ28፥3
35፥27 ዘፀ25፥2፤ 1ዜና29፥6፡8
35፥28 ዘፀ25፥6
35፥29 ቍ4-9፤ ዘፀ25፥2፤1-7፤ 36፥3፤2ነገ12፥4
35፥31 ቍ35፤2ዜና2፥7፡14
35፥34 ዘፀ31፥6፤2ዜና2፥14
35፥35 ቍ31
36፥1 ዘፀ28፥3፤ 25፥8
36፥2 ዘፀ25፥2፤ 31፥2፡6፤
36፥3 ዘፀ35፥29
36፥5 2ዜና24፥ 14፤31፥10፤ 2ቆሮ8፥2-3
36፥7 1ነገ7፥47
36፥13 ቍ18

[a]9 ቁመቱ 1.1 ሜትር፣ ወርዱ 1.8 ሜትር ይሆል ማለት ነው።
[a]15 ቁመቱ 13.5 ሜትር፣ ወርዱ 1.8 ሜትር ያሀል ማለት ነው።

*36፥1-38፤ የ35፥4-39፥43 ማብ ይመ።*

መጋረጃ ጠርዝ አምሳ ቀለበቶችን አበጁ:: [18]ድንኳኑን አንድ ወጥ አድርጎ ለማያያዝም አምሳ የናስ ማያያዣዎችን ሠሩ:: [19]ከዚያም ለድንኳኑ መሸፈኛ የሚሆን ቀይ ከተነከረ የአውራ በግ ቆዳ ሠሩ፤ በላዩ ላይ የሚሆንም የአቆስጣ ቆዳ[a] አበጁ::

[20]ለማደሪያው ድንኳን ከግራር ዕንጨት ወጋግራዎችን አበጁ:: [21]እያንዳንዱም ወጋግራ ቁመቱ ዐሥር ክንድ፣ ስፋቱ አንድ ክንድ ተኩል[b] ነበር፣ [22]ትይዩ የሆኑ ሁለት ጒጦች ነበሩት፤ የማደሪያውን ድንኳን ወጋግራዎች በዚህ መልክ ሠሩ:: [23]በደቡብ በኩል ላለው የማደሪያው ድንኳን ሃያ ወጋግራዎችን አበጁ፤ [24]ለእያንዳንዱ ጒጠት አንድ መቆሚያ፣ ለእያንዳንዱም ወጋግራ ሁለት መቆሚያ ሆኖ አርባ የብር መቆሚያዎችን አበጁ:: [25]በስተሰሜን በኩል ላለው የማደሪያ ድንኳን ሃያ ወጋግራዎችን ሠሩ፤ [26]ለእያንዳንዱ ወጋግራ ሁለት መቆሚያ የሆኑ አርባ የብር መቆሚያዎችን ሠሩ:: [27]በዳር በኩል ይኸውም በስተ ምዕራብ ጫፍ ባለው ማደሪያ ድንኳን ስድስት ወጋግራዎችን ሠሩ:: [28]ዳርና ዳር ላሉት የማደሪያው ድንኳን ማእዘኖችም ሁለት ወጋግራዎችን ሠሩ:: [29]በእነዚህ ሁለት ማእዘኖች ላይ ከታች አንሥቶ እስከ ላይ ድረስ ወጋግራዎቹ በአንድ ላይ ተነባብረው በአንድ ቀለበት ውስጥ ተገጥመው ነበር፤ ሁለቱም አንድ አካል ሆነው ተሠርተው ነበር:: [30]ስለዚህ ስምንት ወጋግራዎችና ለእያንዳንዱም ወጋግራ ሁለት መቆሚያዎች ሆነው ዐሥራ ስድስት የብር መቆሚያዎች ነበሩ::

[31]እንደዚሁም ከግራር ዕንጨት አግዳሚዎችን ሠሩ፤ በማደሪያው ድንኳን በአንድ በኩል ላሉት ወጋግራዎች አምስት አግዳሚዎችን ሠሩ፤ [32]በሌላ በኩል ላሉት አምስት አግዳሚዎች፣ በምዕራብ በኩል በማደሪያው ድንኳን ዳር ላይ ላሉት ወጋግራዎች አምስት አግዳሚዎችን ሠሩ:: [33]በወጋግራዎቹ መካከል ከዳር እስከ ዳር እንዲዘረጋ ሆኖ መካከለኛውን አግዳሚ ሠሩ:: [34]ወጋግራዎቹን በወርቅ ለበጧቸው፤ አግዳሚዎቹን ለመያዝም የወርቅ ቀለበቶችን ሠሩ፤ እንዲሁም አግዳሚዎቹን በወርቅ ለበጧቸው::

[35]ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ፣ በእጅ ጥበብ ባለሙያ ኪሩቤል የተጠለፉበት መጋረጃ አበጁ:: [36]ለእርሱም አራት ምሰሶዎች ከግራር ዕንጨት ሠርተው በወርቅ ለበጧቸው፤ ለእነርሱም አራት የወርቅ ኰላቦችንና አራት የብር መቆሚያዎችን አበጁላቸው:: [37]በድንኳኑ መግቢያ ጥልፍ ጠላፊ እንደሚሠራው ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ መጋረጃ አበጁለት፤ [38]ለእነርሱም ኰላቦች ያሏቸው አምስት ምሰሶዎች ሠሩላቸው፤ የምሰሶዎቹን አናቶችና ዘንጎች በወርቅ በመለበጥ አምስቱን መቆሚያዎች ከነሐስ ሠሩ::

36፥18 ቍ13
36፥35 ዘፀ39፥38፤ ማቴ27፥51፤ሉቃ23፥45፤ዕብ9፥3
36፥37 ዘፀ27፥16

## የኪዳኑ ታቦት

37፥1-9 ተጓ ምብ - ዘፀ 25፥10-20

37 ባስልኤል ርዝመቱ ሁለት ክንድ ተኩል፣ ወርዱ አንድ ክንድ ተኩል[c]፣ ከፍታው አንድ ክንድ ተኩል የሆነ ታቦት ከግራር ዕንጨት ሠራ:: [2]በውስጥና በውጭ በንጹሕ ወርቅ ለበጠው፤ በዙሪያውም የወርቅ ክፈፍ አበጀለት:: [3]አራት የወርቅ ቀለበቶችን ሠርቶ ሁለት ቀለበቶችን በአንድ በኩል፣ ሁለት ቀለበቶችንም በሌላ በኩል አድርጎ ከአራቱ እግሮቹ ጋር አያያዛቸው:: [4]ከዚያም መሎጊያዎችን ከግራር እንጨት ሠርቶ በወርቅ ለበጣቸው:: [5]መሎጊያዎቹንም መሸከሚያ እንዲሆኑ በታቦቱ ጐንና ጐን ባሉት ቀለበቶች ውስጥ አስገባቸው::

[6]ርዝመቱ ሁለት ክንድ ተኩል[d]፣ ወርዱም አንድ ክንድ ተኩል የሆነ ከንጹሕ ወርቅ የስርየት መክደኛ ሠራ:: [7]ከዚያም ከተቀጠቀጠ ወርቅ ሁለት ኪሩቤልን ከመክደኛው ጫፎች ላይ ሠራ:: [8]አንዱን ኪሩብ በአንዱ ጫፍ ላይ፣ ሁለተኛውንም ኪሩብ በሌላው ጫፍ ላይ ሠራ፤ ከሁለቱ ጫፎች ላይ ከክዳኑ ጋር አንድ ወጥ አድርጎ ሠራቸው፤ [9]ኪሩቤልም የስርየት ክዳኑን በመሸፈን ክንፋቸውን ወደ ላይ ዘርግተው ነበር፤ ኪሩቤል ወደ ስርየት መክደኛው እየተመለከቱ እርስ በርሳቸው ገጽ ለገጽ ነበሩ::

## የኅብስት ማስቀመጫው ጠረጴዛ

37፥10-16 ተጓ ምብ - ዘፀ 25፥23-29

[10]ርዝመቱ ሁለት ክንድ፣ ወርዱ አንድ ክንድ፣ ከፍታውም ክንድ ተኩል የሆነ ጠረጴዛ ከግራር እንጨት ሠሩ[e]:: [11]ከዚያም በንጹህ ወርቅ በመለበጥ በዙሪያው የወርቅ ክፈፍ አበጁለት:: [12]በዙሪያውም ስፋቱ አንድ ስንዝር[f] የሆነ ጠርዝ በማበጀት በጠርዙ ላይ የወርቅ ክፈፍ አደረጉበት:: [13]ለጠረጴዛው አራት የወርቅ ቀለበቶች አበጅተው አራቱ እግሮች ካሉበት ከአራቱ ማእዘኖች ጋር አያያዟቸው:: [14]ጠረጴዛውን ለመሸከም የሚያገለግሉትን መሎጊያዎች እንዲይዙ ቀለበቶቹ ከጠርዙ አጠገብ ሆኑ:: [15]ጠረጴዛውን ለመሸከም የሚያገለግሉት መሎጊያዎች ከግራር ዕንጨት የተሠሩና በወርቅ የተለበጡ ነበሩ:: [16]የጠረጴዛውን ዕቃዎች ይኸውም ዝርግ ሳሕኖችን፣ ድስቶችንና ጒድጓዳ ሳሕኖችን እንዲሁም የመጠጥ መሥዋዕቱ ማፍ

37፥1 ዘፀ30፥6፤ 31፥2፤39፥35፤ ዘዳ10፥3
37፥2 ቍ11፥26
37፥6 ዘፀ26፥34፤ 31፥7፤ዕብ9፥5
37፥7 ሕዝ41፥18
37፥9 ዘዳ10፥3፤ዕብ9፥5
37፥10 ዕብ9፥2
37፥11 ቍ2
37፥14 ቍ27

[a]19 ይህ የባሕር አውሬ ነው::
[b]21 ቁመቱ 4.5 ሜትር ወርዱ 0.7 ሜትር ያህል ማለት ነው::
[c]1 ከፍታው 1.1 ሜትር ወርዱና ርዝመቱ 0.7 ሜትር ያህል ማለት ነው::
[d]6 ርዝመቱ 1.1 ሜትር ወርዱ 1.1 ሜትር ያህል ማለት ነው::
[e]10 በዚህና በቍጥር 11-29 ባሉት ክፍሎች፣ሥሩ ተብሎ መተርጐም ይቻላል::
[f]12 ወደ 8 ሳንቲ ሜትር ያህል ማለት ነው::

*37፥1-29* የ35፥4-39፥43 ማብ ይመ::
37፥1 *ባስልኤል ታቦት ሠራ፤* ዋናው የእጅ ጥበብ ባለሙያ (31፥2-3 ይመ)፣ በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከሚቀመጡት ዕቃዎች መካከል እጅግ የተቀደሰውን ዕቃ ለመሥራት ክብር አገኘ፤

ሰኛ የሆኑትን ማንቈርቈሪያዎች ከንጹሕ ወርቅ ሠሯቸው።

**መቅረዙ**
37፥17-24 ተጓ ምብ - ዘፀ 25፥31-39

[17]መቅረዙን ከንጹሕ ወርቅ ሠሩት፤ መቆሚያውንና ዘንጉን ቀጥቅጠው አበጁት፤ የአበባ ቅርጽ ያላቸው ጽዋዎች፣ እንቡጦችና የፈኩ አበቦች ከእርሱ ጋር አንድ ወጥ ሆነው ተሠርተው ነበር። [18]ሦስቱ በአንድ በኩል ሦስቱ በሌላ በኩል በመሆን ስድስት ቅርንጫፎች ከመቅረዙ ጐኖች ተሠርተው ነበር። [19]ከእንቡጦችና ከፈኩ አበቦች ጋር የለውዝ አበባ የሚመስሉ ሦስት ጽዋዎች በአንዱ ቅርንጫፍ ላይ፣ ሦስቱ ደግሞ በሚቀጥለው ቅርንጫፍ ላይ ነበሩ፤ ከመቅረዙ ለወጡት ለስድስቱም ቅርንጫፎች ሁሉ እንዲሁ ነበር። [20]እንቡጦችና የፈኩ አበቦች ያሉባቸው የለውዝ አበባ የሚመስሉ አራት ጽዋዎች በመቅረዙ ላይ ነበሩ። [21]አንደኛው እንቡጥ ከመቅረዙ ወጣ ብለው በሚገኙት በመጀመሪያው ጥንድ ቅርንጫፎች ሥር ሁለተኛውም እምቡጥ በሁለተኛው ጥንድ ሥር እንዲሁም ሦስተኛው እንቡጥ በሦስተኛው ጥንድ ሥር ነበር፣ በስድስቱም ቅርንጫፎች እንዲሁ ነበር። [22]እንቡጦቹና ቅርንጫፎቹ ሁሉ ከንጹሕ ወርቅ ተሠርተው ከመቅረዙ ጋር አንድ ወጥ ነበሩ።

[23]የመቅረዙን ሰባት መብራቶች፣ እንዲሁም መኮስተሪያዎችንና የኮስታሪ ማስቀመጫዎችን ከንጹሕ ወርቅ ሠሩ። [24]መቅረዙንና ዕቃዎቹን ሁሉ ከአንድ መክሊት[ሙ] ንጹሕ ወርቅ ሠሩ።

**የዕጣን መሠዊያው**
37፥25-28 ተጓ ምብ - ዘፀ 30፥1-5

[25]የዕጣን መሠዊያውን ከግራር እንጨት ሠሩ፤ ርዝመቱ አንድ ክንድ፣ ወርዱ፣ አንድ ክንድ፣ ከፍታው ሁለት ክንድ[ሠ] ነበር፤ ቀንዶቹም ከእርሱ ጋር አንድ ወጥ ሆነው ተሠርተው ነበር። [26]ላዩን፣ ጐኖቹን ሁሉና ቀንዶቹን በንጹሕ ወርቅ ለበጧቸው፤ በዙሪያው የወርቅ ክፈፍ አበጁ። [27]ለሽክም የሚሆኑትን መሎጊያዎች ለመያዝ ትይዩ የሆኑ ከክፈፉ ሥር ሁለት የወርቅ ቀለበቶችን ሠሩ። [28]መሎጊያዎቹን ከግራር እንጨት ሠሩ፤ በወርቅም ለበጧቸው።

[29]እንዲሁም የተቀደሰውን ቅብዐ ዘይትና የሽቶ ቀማሚ ሥራ የሆነውን፣ ንጹሕና መልካም መዐዛ ያለውን ዕጣን ሠሩ።

**የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያ**
38፥1-7 ተጓ ምብ - ዘፀ 27፥1-8

**38** ከፍታው ሦስት ክንድ[ረ] የሆነ የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያ ከግራር እንጨት ሠሩ[ሰ]፤ ርዝመቱ አምስት ክንድ፣ ወርዱ አምስት ክንድ የሆነ ባለ ዐራት ማእዘን ነበረ። [2]ቀንዶቹና መሠዊያው አንድ ወጥ ይሆኑ ዘንድ በአራቱም ማእዘኖች ላይ አራት ቀንድ ሠሩ፣ መሠዊያውንም በናስ ለበጡት። [3]ዕቃዎቹንም ሁሉ ይኸውም ምንቸቶቹን፣ መጫሪያዎቹን፣ መርጫ ጐድጓዳ ሳህኖቹን፣ ሜንጦዎቹንና የእሳት መያዣዎቹን ከናስ ሠሯቸው። [4]ለመሠዊያውም ከጠርዝ በታች ሆኖ ከመሠዊያው ግማሽ ቁመት ላይ የሚሆን የናስ ፍርግርግ ማንደጃ ሠሩ። [5]ለናሱ ፍርፍርግ ማንደጃ አራት ማእዘኖች መሎጊያዎቹን እንዲይዙ የናስ ቀለበቶችን ሠሩ። [6]መሎጊያዎቹን ከግራር እንጨት ሠርተው በናስ ለበጧቸው። [7]መሠዊያውን ለመሸከም በመሠዊያው ጐኖች ይሆኑ ዘንድ መሎጊያዎቹን በቀለበቶቹ ውስጥ አስገቧቸው፤ ውስጡንም ክፍት በማድረግ ከሳንቃዎች ሠሩት።

**የመታጠቢያው ሳሕን**

[8]የናስ መታጠቢያ ሳሕንና የናስ መቆሚያውን በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ ከሚያገለግሉት ሴቶች መስተዋት ሠሩት።

**አደባባዩ**
38፥9-20 ተጓ ምብ - ዘፀ 27፥9-19

[9]ቀጥሎም አደባባዩን ሠሩ፤ የደቡቡ ክፍል ርዝመት አንድ መቶ ክንድ[ሸ] ሲሆን፣ በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ የተሠሩ መጋረጃዎች ነበሩት፤ [10]ሃያ ምሰሶዎችና ሃያ የናስ መቆሚያዎች፣ የብር ኰላቦችና በምሰሶዎቹ ላይ ዘንጎች ነበሩት። [11]የሰሜኑም ክፍል ቁመቱ አንድ መቶ ክንድ ነበር፤ ሃያ ምሰሶዎችና ሃያ የናስ መቆሚያዎች፣ የብር ኰላቦችና በምሰሶዎቹም ላይ ዘንጎች ነበሩት።

[12]የምዕራቡ ጫፍ ወርዱ አምሳ ክንድ[ተ] ነበር፤ ዐሥር ምሰሶዎችና ዐሥር መቆሚያዎች እንዲሁም የብር ኰላቦችና በምሰሶዎቹም ላይ ዘንጎች ያሉት መጋረጃዎች ነበሩት። [13]በፀሐይ መውጫ በኩል ያለው የምሥራቁም ጫፍ ወርዱ አምሳ ክንድ ነበር። [14]ከሦስት ምሰሶዎችና ከሦስት መቆሚያዎች ጋር ርዝመታቸው ዐሥራ አምስት ክንድ[ቀ] የሆነ መጋረጃዎች በአንድ በኩል ባለው መግቢያ ላይ ነበሩ፤ [15]ከሦስት ምሰሶዎችና ከሦስት መቆሚያዎች ጋር ርዝመታቸው ዐሥራ አምስት ክንድ የሆኑ መጋረጃዎች በአደባባዩ መግቢያ በሌላው በኩል ነበሩ።

[16]በአደባባዩ ዙሪያ ያሉት መጋረጃዎች በሙሉ በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ የተሠሩ ነበሩ። [17]የምሰሶዎቹ መቆሚያዎች ናስ ነበሩ፤ ኰላቦቹና በምሰሶዎቹ ላይ ያሉት ዘንጎች

37፥17 ዕብ9፥2፤ ራእ1፥12
37፥22 ቍ17፤ ዘኍ8፥4
37፥23 ዘፀ40፥4፡25
37፥25 ዘፀ27፥2፤ 30፥34-36፤ ሉቃ1፥11፤ዕብ9፥4፤ ራእ8፥3፤9፥13
37፥27 ቍ14
37፥28 ዘፀ25፥13
37፥29 ዘፀ31፥11፤ 30፥1፡25፤39፥38
38፥2 2ዜና1፥5
38፥3 ዘፀ31፥9
38፥8 ዘፀ30፥18፤ 40፥7፤ዘጸ23፥17፤ 1ሳሙ2፥22፤ 1ነገ14፥24

[ሙ]24 ወደ 34 ኪሎ ግራም ያህል ማለት ነው።
[ሠ]25 ርዝመቱ ወርዱ 0.5 ሜትር ከፍታው 0.9 ሜትር ያህል ማለት ነው።
[ረ]1 ርዝመቱ 1.3 ሜትር ያህል ማለት ነው።
[ሰ]1 ወይም ሥራ ተብሎ
[ሸ]9 ወደ 46 ሜትር ያህል ነው።
[ተ]12 ወደ 23 ሜትር ያህል ነው።
[ቀ]14 ወደ 6.9 ሜት ያህል ነው።

(25፥10 እና ማብ ይመ)።
*38፥1-31፤* የ35፥4-39፥43 ማብ ይመ።
38፥8 *የናስ ... መስተዋት፤* በጥንት ዘመን ከብርጭቆ የተሠሩ መስተዋቶች የሉም፤ ሆኖም እጅግ በጣም የተወለወሉ የናስ መስተዋቶች ምስልን በበቂ ሁኔታ መልሰው ያንጸባርቁ ነበር። *መገናኛ ድንኳን፤* የ27፥21 ማብ ይመ።

ከብር የተሠሩ ነበሩ፤ ጫፎቻቸውም በብር ተለብጠው ነበር፤ ስለዚህ የአደባባዩ ምሰሶዎች ሁሉ የብር ዘንጎች ነበሯቸው::

[18]በአደባባዩ መግቢያ ላይ ያለው መጋረጃ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊ፣ ከቀይ ማግና የጥልፍ ባለሙያ ከጠለፈው፣ በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ የተሠራ ነበር፤ ቁመቱ ሃያ ክንድ[ተ]፣ እንደ አደባባዩ መጋረጃዎች ከፍታው አምስት ክንድ ነበረ፤ [19]አራት ምሰሶዎችና አራት መቆሚያዎች ነበሩት፤ ኵላቦቻቸውና ዘንጎቻቸው የብር ሲሆኑ፣ ጫፎቻቸው በብር ተለብጠው ነበር:: [20]የማደሪያው ድንኳንና የአደባባዩ ዙሪያ ካስማዎች ሁሉ ከናስ የተሠሩ ነበሩ::

## ለአገልግሎት የዋሉ ዕቃዎች

[21]ለማደሪያው ድንኳን፣ ይኸውም ለምስክሩ ድንኳን ሙሴ ባዘዘው፣ በካህኑ በአሮን ልጅ በኢታማር መሪነት ሌዋውያኑ በጻፉት መሠረት የዕቃዎቹ ቍጥር ይህ ነው:: [22]ከይሁዳ ነገድ የሆር የልጅ ልጅ፣ የኡሪ ልጅ የሆነው ባስልኤል፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ያዘዘውን ሁሉ አደረገ:: [23]ከእርሱም ጋር ከዳን ነገድ የሆነው የአሂሳሚክ ልጅ ኤልያብ፣ ዕቅድ አውጭና የእጅ ጥበብ ባለሙያ፣ በሰማያዊ፣ በሐምራዊ፣ በቀይ ማግና በቀጭን በፍታ ጥልፍ ጠላፊ ነበር:: [24]ለመቅደሱ ሥራ ሁሉ ከመወዝወዙ ስጦታ በመቅደሱ ሰቅል መሠረት የዋለው ጠቅላላ ወርቅ ሃያ ዘጠኝ መክሊትና ሰባት መቶ ሠላሳ ሰቅል[ቸ] ነበረ::

[25]በቈጠራው ወቅት ተቈጥረው ከነበሩት ማኅበረሰብ የተገኘው ብር ለመቅደሱ ሰቅል አንድ መቶ መክሊትና አንድ ሺህ ሰባት መቶ ሰባ አምስት ሰቅሎች[ኀ] ነበሩ፤ [26]ከተቈጠሩት ጋር አብረው ከሆኑት ሃያና ከሃያ ዓመት በላይ የሆናቸው ስድስት መቶ ሦስት ሺህ አምስት መቶ አምሳ ሰዎች የሰጡት እንደ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን በአንድ ሰው አንድ ቤካ ይኸውም ግማሽ ሰቅል[ነ] ነበረ:: [27]አንድ መቶ የብር መክሊቶች[ኘ] የመቅደሱንና የመጋረጃዎቹን መቆሚያዎች ለመሥራት አገልግሎት ላይ ውለው ነበር፤ ይኸውም ከአንድ መቶ መክሊቶች አንድ መቶ መቆሚያዎች ሲሆን፣ ለእያንዳንዱ መቆሚያ አንድ መክሊት ማለት ነው:: [28]አንድ ሺህ ሰባት መቶ ሰባ አምስት ሰቅሎችን[አ] ለምሰሶዎቹ ኵላቦች፣ የምሰሶዎቹን አናት ለመለበጥና ዘንጎቻቸውንም ለመሥራት አገልግሎት ላይ ውለው ነበር::

[29]ከመወዝወዙ ስጦታ የሆነው ናስ ሰባ መክሊትና ሁለት ሺህ አራት መቶ ሰቅል[ከ] ነበረ:: [30]ለመገናኛው ድንኳን መግቢያ ለናስ መሠዊያው ከናስ መጫሪያው፣ ለዕቃዎቹም ሁሉ መቆሚያዎቹን ለመሥራት አገልግሎት ላይ አውለውት ነበር፤ [31]ለአደባባዩ ዙሪያ፣ ለመግቢያው እንዲሁም ለማደሪያው ድንኳን ካስማዎች ሁሉና ለአደባባዩ ዙሪያ ሁሉ እንዲሁ አገልግሎት ላይ አውለውት ነበር::

38፥20 ዘፀ35፥18
38፥21 ዘኍ1፥50፡ 53፤4፥28፡33፤8፥24፤ 9፥15፤10፥11፤17፥7፤ 1ዜና23፥32፤ 2ዜና24፥6፤ ሐሥ7፥44፤ራእ15፥5
38፥22 ዘፀ31፥2
38፥23 ዘፀ31፥6
38፥24 ዘፀ30፥13፡ 16
38፥25 ዘፀ30፥12
38፥26 ዘፀ12፥37፤ 30፥12፡13፡14፤
38፥27 ዘፀ26፥19

## የክህነት አልባሳት

**39** ለመቅደሱ አገልግሎት ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ የተፈተሉ ልብሶችን ሠሩ፤ እንዲሁም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው ለአሮን የተቀደሱ ልብሶችን ሠሩ::

### ኤፉድ
39፥2-7 ተጓ ምብ - ዘፀ 28፥6-14

[2]ኤፉዱን ከወርቅ፣ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ፣ በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ ሠሩት[ኸ]፤ [3]ጥበበኛ ባለሙያ እንደሚሠራው በሰማያዊ፣ በሐምራዊ፣ በቀይ ማግና በቀጭን በፍታ ይሠራ ዘንድ ወርቁን በስሱ ቀጥቅጠው እንደ ክር ቈራረጡት:: [4]ለኤፉዱ ከሁለቱ ጐኖቹ ጋር ተያይዘው ያሉትን የትከሻ ንጣዮችን ሠሩ፤ ይኸውም ማያያዝ እንዲቻል ነው:: [5]በጥበብ የተፈተለው መታጠቂያ በተመሳሳይ መልክ ሆኖ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው፣ ከኤፉዱ ጋር አንድ ወጥ የሆነና ከወርቅ፣ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ፣ በቀጭኑ ከተፈተለ ሐር የተሠራ ነበረ::

[6]የከበሩ መረግዶችን በወርቅ ፈርጦች በመክፈፍ፣ እንደ ማኅተም የእስራኤልን ልጆች ስሞች ቀረጹባቸው:: [7]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው በኤፉዱ የትከሻ ንጣዮች ላይ ለእስራኤል ልጆች እንደ መታሰቢያ ድንጋዮች አያያዟቸው::

### የደረት ኪስ
39፥8-21 ተጓ ምብ - ዘፀ 28፥15-28

[8]የደረት ኪሱንም ጥበበኛ ባለሙያ እንደሚሠራው ሥራ በተመሳሳይ መንገድ ሠሩት፤ እንደ ኤፉዱም ከወርቅ፣ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ በቀጭኑም ከተፈተለ በፍታ ሠሩት:: [9]ርዝመቱ አንድ ስንዝር ወርዱም አንድ ስንዝር[ወ] ሲሆን፣ ጥንድ

39፥1 ቍ41፤ ዘፀ28፥2፤35፥19፡23
39፥7 ዘሌ24፥7፤ ኢያሱ4፥7
39፥8 ዘሌ8፥8

[ተ]18 ወደ 9 ሜትር ያህል ነው::
[ቸ]24 የወርቁ መጠን ወደ አንድ ሜትሪክ ቶን ያህል ነው::
[ኀ]25 የብሩ መጠን 3.4 ሜትሪክ ቶን ያህል ነው::
[ነ]26 ወደ 5.5 ግራም ያህል ነው::
[ኘ]27 ወደ 3.4 ሜትሪክ ቶን ያህል ነው::
[አ]28 ወደ 20 ኪሎ ግራም ያህል ነው::
[ከ]29 የናሱ መጠን 2.4 ሜትሪክ ቶን ያህል ነው::
[ኸ]2 በዚህ እንዲሁም በቍጥር 7፡8 እና 22 ላይ፣ ሥራ ተብሎ መተርጐም ይችላል::
[ወ]9 ወደ 22 ሳንቲ ሜትር ያህል ነው::

38፥25 *አንድ መቶ መክሊትና አንድ ሺህ ሰባት መቶ ሰባ አምስት ሰቅሎች፤* በሌላ አነጋገር 100 መክሊት 1,775 ሰቅል ነበር፤ አንድ መክሊት 3,000 ሰቅል ሲሆን፣ 100 መክሊት 300,000 ሰቅል ይሆናል፤ በጠቅላላው ሕዝቡ የሰጠው 301,775 ሰቅል ነው፤ ይህም ለእያንዳንዱ ዘማች ወንድ ግማሽ ሰቅል ይደርሳል፤ (ቍ26)::

38፥26 *ስድስት መቶ ሦስት ሺህ አምስት መቶ ኀምሳ፤* ይህ ቍጥር እንዳለ ሊወሰድ ስለመቻሉ አጠራጣሪ አይደለም:: ምክንያቱም በነገድ ቈጠራው ጊዜ ጠቅላላ ቍጥራቸው 603,550 (ዘኍ 1፥21-43፡2፥4-31) ነበር፤ (የዘኍ1፥46 እና ማብ ይመ)::

38፥27 *አንድ መቶ የብር መክሊቶች፤* የ26፥19 ማብ ይመ::

*39፥1-43፤* የ35፥4-39፥43 ማብ ይመ::

ድርብ ሆኖ ባለ አራት ማእዘን ነበረ:: [10]ከዚያም የከበሩ ድንጋዮችን በአራት ረድፍ በላዩ ላይ አደረጉበት፤ በመጀመሪያው ረድፍ ሰርድዮን፣ ቶጳዝዮንና የሚያብረቀርቅ ዕንቍ ነበር፤ [11]በሁለተኛው ረድፍ በሉር፣ ሰንፔርና° አልማዝ፣ [12]በሦስተኛው ረድፍ ያክንት፣ ኬልቄዶንና አሜቴስጢኖስ፣ [13]በአራተኛው ረድፍ ቢረሌ፣ መረግድና ኢያስጲድ" ነበረ፤ በወርቅ ፈርጥ ላይ ተደርገው ነበር:: [14]ለእያንዳንዱ የእስራኤል ልጆች ስም አንዳንድ ሆኖ፣ በእያንዳንዱ ላይ እንደ ማኅተም ከዐሥራ ሁለቱ ነገዶች የአንዱ ስም የተቀረጸበት ዐሥራ ሁለት ድንጋዮች ነበሩ::

[15]ለደረት ኪሱም ልክ እንደ ገመድ ከንጹሕ ወርቅ የተጐነጐኑ ድሪዎችን አበጁለት:: [16]ሁለት የወርቅ ፈርጦችንና ሁለት የወርቅ ቀለበቶችን ሠርተው ቀለበቶቹን ከደረት ኪሱ ሁለት ጐኖች ጋር አያያዟቸው:: [17]ሁለቱን የወርቅ ድሪዎች በደረት ኪሱ ጐንና ጐን ካሉት ቀለበቶች ጋር አያያዟቸው፤ [18]የድሪዎቹን ሌሎች ጫፎች ከፊት ካለው ከኤፉዱ የትከሻ ንጣዮች ጋር በማገናኘት ከሁለቱ የወርቅ ፈርጦች ጋር አያያዟቸው:: [19]ሁለት የወርቅ ቀለበቶችን ሠርተው ከኤፉዱ ቀጥሎ ካሉት ከሌሎቹ ሁለት የደረት ኪስ ጐኖች ጋር ከውስጠኛው ጠርዝ ላይ አያያዟቸው:: [20]ከዚያም ሁለት ተጨማሪ የወርቅ ቀለበቶችን ሠርተው ልክ ከኤፉዱ መታጠቂያ በላይ፣ ከመጋጠሚያው አጠገብ፣ ከኤፉዱ ፊት ለፊት ካሉት ከትከሻ ንጣዮች ጋር አያያዟቸው:: [21]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው የደረት ኪሱ ከኤፉዱ ተነጥሎ ለብቻው እንዳይንጠለጠል የደረት ኪሱን ቀለበቶች ከመታጠቂያው ጋር በማገናኘት፣ ከኤፉዱ ቀለበቶች ጋር በሰማያዊ ፈትል አሠሯቸው::

## ሌሎች የክህነት አልባሳት

39፥22-31 ተጓ ምብ - ዘፀ 28፥31-43

[22]የኤፉዱን ቀሚስ በሸማኔ ሥራ ሙሉ በሙሉ ከሰማያዊ ጨርቅ ሠሩት፤ [23]ይህም እንደ ክሳዱ ቅድ ከቀሚሱ መካከል ላይ አንገትጌ" ነበረው፤ እንዳይተረተርም በዐንገትጌው ዙሪያ ላይ ቅምቅማት ነበረው:: [24]በቀሚሱ ጠርዝ ዙሪያ ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ እንዲሁም በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታ ላይ ሮማኖቹን አደረጉ:: [25]ከንጹሕ ወርቅም ሻኵራዎችን ሠሩ፤ እነዚህንም በሮማኖቹ መካከል በጠርዙ ዙሪያ አደረጉ:: [26]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው ለአገልግሎት ይለበስ ዘንድ ሻኵራዎቹና ሮማኖቹ በቀሚሱ ጠርዝ ዙሪያ ላይ ተሰባጥረው ይገኙ ነበር::

[27]ለአሮንና ለወንዶች ልጆቹ የሸማኔ ሥራ የሆነውን ከቀጭን በፍታ ሸሚዞችን ሠሩ፤ [28]እንዲሁም ከቀጭን በፍታ ጥምጥምን፣ የሐር ቆብቹንና በቀጭኑ ከተፈተለም በፍታ ሱሪዎችን ሠሩ:: [29]መታጠቂያው እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው በቀጭኑ ከተፈተለ በፍታና ከሰማያዊ፣ ከሐምራዊና ከቀይ ማግ፣ የጥልፍ ጠላፊ ሥራ ሆኖ የተሠራ ነበረ::

[30]ከንጹሕ ወርቅ የተቀደሰውን አክሊል ሰሌዳ ሠርተው፣ በማኅተም ላይ እንደ ተቀረጸ ጽሑፍ፣ "ቅዱስ ለእግዚአብሔር (ያህዌ)" የሚል ቀረጹበት፤ [31]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው ከመጠምጠሚያው ጋር ለማያያዝ ሰማያዊ ፈትል አሠሩበት::

## ሙሴ የማደሪያውን ድንኳን መቈጣጠሩ

39፥32-41 ተጓ ምብ - ዘፀ 35፥10-19

[32]በዚህ መሠረት የማደሪያው ድንኳን፣ የመገናኛው ድንኳን ሥራ በሙሉ ተጠናቀቀ፤ እስራኤላውያን ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው ሁሉን ነገር ሠሩ:: [33]ከዚያም የማደሪያውን ድንኳን ወደ ሙሴ አመጡት፤ እነዚህም ድንኳንና ዕቃዎቹን ሁሉ፣ ማያያዣዎቹ፣ ክፈፎቹ፣ አግዳሚዎቹ፣ ምሰሶዎቹና መቆሚያዎቹ፤ [34]ቀይ ከተነከረ የአውራ በግ ቆዳ የተሠራ መደረቢያ፣ የለፋ የአቀስጣ ቆዳ' መደረቢያና መከለያ መጋረጃ፤ [35]የምስክሩ ታቦት፣ ከመሎጊያዎቹና ከስርየት መክደኛው ጋር፤ [36]ጠረጴዛው ከዕቃዎቹ ሁሉና ከኅብስተ ገጽ ጋር፤ [37]ከንጹሕ ወርቅ የሆነው መቅረዝ ከተደረደሩት መብራቶችና ከዕቃዎቹ ሁሉ ጋር፣ የመብራቱም ዘይት፣ [38]የወርቅ መሠዊያው፣ ቅብዐ ዘይቱ፣ መልካም መዐዛ ያለው ዕጣን እንዲሁም የድንኳኑ መግቢያ መጋረጃ፣ [39]የናስ መሠዊያው ከናስ መጫሪያው፣ መሎጊያዎቹና ዕቃዎቹ ሁሉ ጋር፣ የመታጠቢያው ሳሕን ከነማስቀመጫው፣ [40]የአደባባዩ መጋረጃዎች ከምሰሶዎቹና ከመቆሚያዎቹ ጋር፣ የአደባባዩ መግቢያ መጋረጃ፣ ገመዶቹና የአደባባዩ የድንኳን ካስማዎች፣ የማደሪያው፣ የመገናኛው ድንኳን ዕቃዎች ሁሉ፤ [41]በመቅደሱ ሲያገለግሉ የሚለበሱት የተፈተሉት ቀሚሶች፣ ለካህኑ ለአሮን የተቀደሱት ቀሚሶችና ወንዶች ልጆቹ ክህነት ሆነው ሲያገለግሉ የሚያደርጓቸው ቀሚሶች ናቸው::

[42]እስራኤላውያን ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው ሥራውን ሁሉ አከናወኑ:: [43]ሙሴ ሥራውን አየ፤ ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘው መሥራታቸውንም ተመለከተ፤ ስለዚህ ባረካቸው::

°11 ወይም ላፒስ ላዙሊ
"13 ከእነዚህ የከበሩ ማዕድኖች መካከል አንዳንዶቹ ማንነታቸው አይታወቅም::
"23 በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጉም በትክክል አይታወቅም::
'34 ይህ የባሕር አሳሬ ነው::

39፥14 ራእ21፥12
39፥27 ዘሌ6፥10፤ 8፥2
39፥28 ቍ31፤ ዘፀ28፥4፤ዘሌ8፥9፤ ኢሳ61፥10
39፥30 ኢሳ23፥18፤ ዘካ14፥20
39፥31 ቍ28
39፥32 ዘፀ25፥9
39፥33 ዘፀ25፥8-40፤36፥8-38
39፥35 ዘፀ37፥1
39፥36 ዘፀ25፥23-30፤37፥10-16
39፥37 ዘፀ25፥6:31-39
39፥38 ዘፀ30፥1-10:22-32:34-38፤ 36፥35፤37፥25-29
39፥39 ዘፀ27፥1-8፤ 30፥18፤38፥1-7
39፥40 ዘፀ27፥9-19፤38፥9-20
39፥41 ቍ1
39፥42 ዘፀ25፥9
39፥43 ዘፍ31፥55፤ ዘፀ25፥9፤35፥10፤ ዘሌ9፥22:23፤ ዘኍ 6፥23-27፤ ዘዳ21፥5፤ 26፥15፤2ሳሙ6፥18፤ 1ነገ8፥14:55፤1ዜና 16፥2፤2ዜና30፥27

39፥30 *የተቀደሰውን አክሊል፤* በመጠምጠሚያው ላይ ላለው ቅጠል የተሰጠ ይፋዊ ስም ነው፤ (ይህ ስም በ28፥36-37 ላይ አልተጠቀሰም)::

39፥32 *ሥራ በሙሉ ተጠናቀቀ፤* እግዚአብሔር የሥነ ፍጥረት ሥራውን በጨረሰ ጊዜ የተናገረውን የሚያስታውስ ቃል ነው፤ (ዘፍ 2፥1-3 ይመ)::

39፥43 *ሙሴም ... ባረካቸው፤* እስራኤላውያን የመገናኛ

## የማደሪያውን ድንኳን መትከል

40 ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ [2]"ማደሪያውን ይኸውም የመገናኛውን ድንኳን በወሩ የመጀመሪያ ቀን ትከለው፤ [3]የምስክሩን ታቦት በውስጡ አኑር፤ ታቦቱንም በመጋረጃው ጋርደው። [4]ጠረጴዛውንም ወደ ውስጥ አምጥተህ ዕቃ ዎቹን በላዩ ላይ አሰናዳ፤ ከዚያም መቅረዙን አስገብተህ መብራቶቹን በቦታቸው አስ ቀምጥ። [5]የዕጣኑን የወርቅ መሠዊያ በምስ ክሩ ታቦት ፊት ለፊት አስቀምጠው፤ ከማ ደሪያውም መግቢያ ላይ መጋረጃውን አድርግ።

[6]"የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያውን በማደሪያው መግቢያ ፊት ለፊት፣ በመገ ናኛው ድንኳን አስቀመጠው። [7]የመታጠቢ ያውን ሰን በመገናኛው ድንኳንና በመሠዊ ያው መካከል አኑርበት፤ ውሃም አኑርበት። [8]በዙሪያውም የአደባባዩን ቅጥር ትከል፤ መጋረጃውንም በአደባባዩ መግቢያ ላይ አድ ርገው።

[9]"ቅብዐ ዘይቱን ወስደህ ማደሪያውንና በውስጡ ያለውን ሁሉ ቅባ፤ እርሱንና ዕቃ ውን ሁሉ ቀድስ፤ የተቀደሰም ይሆናል። [10]ከዚያም የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያ ውንና ዕቃዎቹን ሁሉ ቅባ፤ መሠዊያውን ቀድስ እጅግም የተቀደሰ ይሆናል። [11]የመ ታጠቢያው ሰንና ማስቀመጫውን ቅባ፤ ቀድሳቸውም።

[12]"አሮንና ወንዶች ልጆቹን ወደ መገና ኛው ድንኳን መግቢያ አምጥተህ በውሃ እጠባቸው። [13]ከዚያም አሮንን የተቀደሰውን ልብስ አልብሰው፤ ካህን ሆኖ ያገለግለኝ ዘንድ ቅባው፤ ቀድሰውም [14]ወንዶች ልጆቹን አምጥተህ ሸሚዝ አልብሳቸው። [15]ካህናት ሆነው ያገለግሉኝ ዘንድ ልክ አባታቸውን እንደ ቀባህ ቅባቸው፤ መቀባታቸውም በሚ መጡት ትውልዶች ሁሉ ለሚቀጥል ክህ ነት ነው።" [16]ሙሴ ሁሉንም ነገር ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘው አደረገ።

[17]እንዲሁም በሁለተኛው ዓመት፣ የመ ጀመሪያው ወር በገባ በመጀመሪያው ቀን የማደሪያው ድንኳን ተተከለ። [18]ሙሴ የማደሪያውን ድንኳን በተከለ ጊዜ፣ መቆ ሚያዎቹን በቦታቸው አኖረ፤ ወጋግራዎቹን አቆመ አግዳሚዎቹን አስገባ፤ ምሰሶዎቹንም ተከለ። [19]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘ ዘው ድንኳኑን በማደሪያው ላይ፣ መደረቢ ያውንም በድንኳኑ ላይ ዘረጋው።

[20]ምስክሩን ወስዶ በታቦቱ ውስጥ አስቀ መጠው፤ መሎጊያዎቹንም ከታቦቱ ጋር አያያዛቸው፤ የስርየት መክደኛውንም በላዩ ላይ አደረገው። [21]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘው ታቦቱን ወደ ማደሪያው ድን ኳን አስገብቶ መከለያ መጋረጃውን ሰቀለ፤ የምስክሩንም ታቦት ጋረደው።

[22]ሙሴ ጠረጴዛውን በመገናኛው ድንኳን ውስጥ፣ ከማደሪያው በስተ ሰሜን ከመጋረ ጃው ውጭ አኖረው፤ [23]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘውም ኅብስቱን በላዩ ላይ በእግዚ አብሔር (ያህዌ) ፊት አኖረ።

[24]መቅረዙን በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከጠረጴዛው ትይዩ ከማደሪያው ድንኳን በስተ ደቡብ በኩል አኖረው፤ [25]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘውም መብራቶቹን በእግዚአ ብሔር (ያህዌ) ፊት አበራ።

[26]ሙሴ የወርቅ መሠዊያውን በመገና ኛው ድንኳን ውስጥ ከመጋረጃው ፊት ለፊት አኖረው፤ [27]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳ ዘዘውም መልካም መዐዛ ያለውን ዕጣን አጠ ነበት። [28]ከዚያም መጋረጃውን በማደሪያው ድንኳን መግቢያ ላይ ሰቀለው።

[29]የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያውንም በማደሪያው፣ በመገናኛው ድንኳን መግቢያ ላይ አኖረው፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘ ዘውም የሚቃጠለውን መሥዋዕትና የእህ ሉን መሥዋዕት በላዩ ላይ አቀረበ።

[30]የመታጠቢያውን ሰን በመገናኛው ድን ኳንና በመሠዊያው መካከል አስቀመጠ፤ ለመታጠቢያም ውሃ አደረገበት፤ [31]ሙሴና አሮን፣ ወንዶች ልጆቹም እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን ይታጠቡበት ነበር። [32]እግዚ አብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው ወደ መገ ናኛው ድንኳን በገቡና ወደ መሠዊያው በቀረቡ ቍጥር ይታጠቡ ነበር።

[33]ከዚያም ሙሴ በማደሪያውና በመሠዊ ያው ዙሪያ አደባባዩን ተከለ፤ በአደባባዩም መግቢያ ላይ መጋረጃውን ሰቀለ፤ እንደዚህ አድርጐ ሙሴ ሥራውን ፈጸመ።

### የእግዚአብሔር (ያህዌ) ክብር

[34]ከዚያም ደመናው የመገናኛውን ድን ኳን ሸፈነ፤ የእግዚአብሔርም (ያህዌ) ክብር ማደሪያውን ሞላ። [35]ደመናው በላዩ ላይ ስለነበረና የእግዚአብሔርም (ያህዌ) ክብር ማደ ሪያውን ስለሞላው፣ ሙሴ ወደ መገናኛው

40፥2 ቍ 17:34: 35፤ዘፀ12፥2፤26፥30፤ ዘሌ1፥1፤3፥2፤6፥26፤ 9፥23፤16፥16፤ ዘኍ1፥1፤7፥89፤9፥1፤ 11፥16፤17፥4፤20፥6፤ ኢሱ18፥1፤19፥51፤ ኤር7፥12
40፥3 ዘፀ26፥33
40፥4 ዘፀ25፥23: 30:31
40፥5 ዘፀ30፥1
40፥6 ዘፀ27፥1፤ 2ነገ16፥14፤2ዜና4፥1
40፥7 ዘፀ30፥18
40፥8 ዘፀ27፥9
40፥9 ዘፀ30፥26፤ ዘኍ7፥1
40፥10 ዘፀ29፥36
40፥12 ዘፀ29፥4፤ 30፥19፤ዘኍ8፥9
40፥13 ዘፀ28፥41፤ ዘሌ8፥12
40፥14 ዘፀ28፥40፤ ዘሌ10፥5
40፥15 ዘፀ29፥9
40፥16 ዘፍ6፥22
40፥17 ቍ 2፤ ዘኍ7፥1
40፥18 ዘፀ36፥20- 34፤2ዜና1፥3
40፥19 ዘፍ 6፥22፤ዘፀ36፥19
40፥20 ዘፀ16፥34፤ 25፥21፤17-22፤ 26፥34፤31፥7፤ ዕብ9፥4
40፥21 ዘፍ6፥22፤ ዘፀ26፥33
40፥22 ዘፀ25፥23
40፥23 ዘፍ6፥22፤ ዘፀ25፥30፤ ዘሌ24፥5-8፤
40፥24 ዘፀ25፥31
40፥25 ዘፍ6፥22፤ ዘፀ37፥23
40፥26 ዘፀ30፥1
40፥27 ዘፍ6፥22
40፥28 ዘፀ26፥36
40፥29 ዘፍ6፥22፤ ዘፀ20፥24፤29፥38-42
40፥30 ቍ 7፤ዘፀ 30፥18
40፥31 ዘፀ30፥ 19-21
40፥32 ዘፍ6፥22፤ ዘፀ30፥20
40፥33 ዘፀ27፥9: 16፤38፥9-20
40፥34 ዘፀ16፥7፤ 19፥16፤ዘሌ16፥2፤ ዘኍ9፥15-23፤ 1ነገ8፥12፤2ዜና5፥13 ኢሳ6፥4፤ ሐዝ10፥4፤ዮሐ1፥14፤ 12፥41፤ራእ15፥8
40፥35 ዘፀ16፥10፤ 1ነገ8፥11፤2ዜና5፥ 13-14፤7፥2

ውን ድንኳንና ዕቃዎቹን ለመሥራት ስጦታዎቻቸውን፣ ጊዜአቸ ውንና ጉልበታቸውን በታማኝነት ስለሰጡ ተባረኩ፤ ለእግዚአብሔር አገልግሎት ታማኝ ሆኖ መገኘት መለኮታዊ በረከትን ያስገኛል።

40፥2 *በወሩ መጀመሪያ ቀን፤* የፋሲካ በዓል ከተከበረ ከአንድ ዓመት በኋላ የመገናኛው ድንኳን ተተከለ።

40፥16 *ሙሴም ... እግዚአብሔር እንዳዘዘው አደረገ፤* የሙሴ እግዚአብሔርን መታዘዝ የዘጸአት መጽሐፍ የመጨረሻው ምዕራፍ ዋና ሐሳብ ነው፤ (ቍ 19:21:23:25:27:29:32 ይመ)። የመገናኛውን ድንኳን ለመሥራት አስፈላጊ የሆነውን ነገር ሁሉ ያቀረበው ሕዝቡ ቢሆንም፣ ድንኳኑን ለመትከልና ጌታም እንዲ ያድርበት ለማዘጋጀት ሥልጣን የተሰጠው ግን ለእግዚአብሔር ባሪያ ለሙሴ ነው።

40፥33 *ሙሴ ሥራውን ፈጸመ፤* የ39፥32 ማብ ይመ።

*40፥34፤* የእግዚአብሔር ክብር በመገናኛው ድንኳን ላይ እንደ ደመና በረበበና ድንኳኑንም በሞላው ጊዜ፣ እግዚአብሔር በሕዝቡ ታሪክ ውስጥ የሚሠራው ታላቅ ሥራ ለእስራኤል ሕዝብ ከግብፅ መውጣት እንደ ጥላ በሆነው በሙሴ መወለድና በዐባይ ወንዝ መውጣት ከመጨረሻው ከፍተኛ ደረጃ ላይ ደረሰ። ከዚህ በኋላ እስራኤላውያን ምድረ በዳውንና ታሪክን እያቋረጡ በመካ ከላቸው አድሮ መንገዳቸውን በሚያቀናው ጌታ እየተመሩ ፊታቸ ውን ወደ ተስፋዪቱ ምድር አቀኑ።

ድንኳን መግባት አልቻለም።

[36]በእስራኤላውያን ጉዞ ሁሉ ደመናው ከማደሪያው ላይ በተነሣ ጊዜ፣ ይጓዙ ነበር፤ [37]ደመናው ካልተነሣ ግን፣ እስከሚነሣበት ቀን ድረስ አይጓዙም ነበር። [38]ስለዚህ በጕዞ አቸው ሁሉ ወቅት፣ በእስራኤል ቤት ፊት ሁሉ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ደመና በቀን ከማ ደሪያው በላይ፣ በሌሊትም እሳቱ በደመ ናው ውስጥ ነበር።

40፥36 ዘኍ9፥17-23፤10፥13
40፥38 ዘፀ13፥21፤ 1ቆሮ10፥1

*40፥38፤* የ13፥21 ማብ ይመ። *በእስራኤል ቤት፤* ሕዝቡ እንደ አንድ ትልቅ ቤተ ሰብ መታየቱን የሚያሳይ አባባል ነው።

# ኦሪት ዘሌዋውያን

## መግቢያ

### ጸሐፊውና የተጻፈበት ጊዜ

የ1፥1 ማብ እና በኦሪት ዘፍጥረት መግቢያ ሥር "ጸሐፊውንና የተጻፈበት ዘመን" የሚለውን ይመ::

### አሰያየሙ

"ሊቪቲከስ" የሚለው የእንግሊዘኛ ስያሜ የተወሰደው ከሰብዓ ሊቃናት ትርጉም ሲሆን ትርጓሜ ውም "ከሌዋውያን ጋር የተገናኘ" ማለት ነው:: "ዋይቅራ"የሚለው የዕብራይስጡ ስያሜ ደግሞ ከመ ጽሐፉ የመጀመሪያ ቃል የተገኘ ነው:: ትርጉሙም "እርሱ (እግዚአብሔር) ጠርቶ" ማለት ነው::

ዘሌዋውያን መጽሐፍ በመገናኛው ድንኳን ውስጥ በአሮን ልጆች የክህነት አገልግሎት የሚካሄደውንና በሌዋውያን የሚታገዘውን ሥርዐተ አምልኮ የሚያሳይ ነው:: የኦሪት ዘፀአት መጽሐፍ የመገናኛው ድንኳን እንዴት መሠራት እንዳለበት መመሪያ የተሰጠበት ሲሆን፣ የኦሪት ዘሌዋውያን መጽሐፍ ደግሞ በመገናኘው ድንኳን የሚካሄደውን ሥርዐተ አምልኮ ሕግጋት፣ ቀዱስ (በዓላት፣ ስለ ሰባተኛ ዓመትና ኢዮቤልዩ ዓመት ያስተምራል:: ከነዚህ አብዛኞቹ ሕግጋት የተሰጡት እስራኤላውያን በሲና ተራራ በሰፈሩበት ዓመት ነው፤ ይኸውም እግዚአብሔር የጦር ኀይሉን አስተዳደሩን ሥርዐተ አምልኮውን ሙሴ እንዲያደራጅ ባዘዘበት ወቅት ነው:: የኦሪት ዘኍልቅ መጽሐፍ ደግሞ፣ ከሲና ወደ ከነዓን ለመንቀሳቀስ የተደረገውን ዝግጅት ይተርካል::

### መሪ ሐሳቡ

የዚህ መጽሐፍ ዐቢይ ሐሳብ ቅድስና ሲሆን፣ የእግዚአብሔርንና የሰውን ቅድስና ያመለክታል (የ11፥44 ማብ ይመ):: ሰው እግዚአብሔርን በቅድስና ሊያመልከው ይገባል:: በዘሌዋውያን መጽሐፍ መንፈሳዊ ቅድስና በአካላዊ ፍጹምነት ተመስሎአል:: ስለዚህም ለመሥዋዕትነት የሚቀርቡ እንስሳት ፍጹም (ም 1-7) እንዲሁም ካህናቱ ያለነቀፋ መሆን ይጠበቅባቸዋል (ም 8-10)፤ ሴቶች ከወለዱ በኋላ የሚፈሳቸው ደም (ም 12)፣ ደዌና ለምጽ (ም 13-14)፣ ከሰውነት የሚወጣ ፈሳሽ (15፥1-18)፣ የሴቶች የወር አበባ (15፥19-33)፣ እነዚህ ሁሉ የነቀፋ ምልክቶች ተደርገው መወሰዳቸው የሰውን መንፈሳዊ ጒድለት ይወክላሉ:: አዳምና ሔዋን ከኤደን ገነት እንደ ተባረሩ፣ በቆዳ ላይ የሚታይ ማንኛውም በሽታ ያለው ሰው የእግዚአብሔር መገኛ ከሆነው ከሰፈሩ ተለይቶ ይወጣ ነበር:: ይህም ሰው ወደ ሰፈሩ (ወደ እግዚአብሔር መገኛ) የሚመለሰው፣ ከበሽታው መንጻቱ በካህኑ ከተረጋገጠ በኋላ ብቻ ነበር:: ከመመለሱም በፊት የታዘዘውን መሥዋዕት ማቅረብ ግዴታው ነበር (ይህ የክርስቶስን ፍጹም መሥዋዕ ትነት ይወክላል):: በሲና ከተደረገው ኪዳን በኋላ እስራኤል በምድር ላይ የእግዚአብሔርን መንግሥት የምትወክል አገር ስለ ሆነች፣ ንጉሥዋም እግዚአብሔር ስለ ሆነ መተዳደሪያዋን ሁሉ እርሱ መሥርቶአል:: ሃይማኖታዊ፣ ማኅበራዊና ግላዊ ሕይወት ሁሉ የሚመራው እግዚአብሔር ሕዝቡን በቅድስና ለመምራት ባዘጋጀው ሥርዐት መሠረት ነው:: ለሃይማኖታዊ ሥርዐቶች የተለየ ትኵረት ይሰጥ ነበር፤ መሥዋዕቶች የሚቀርቡትም የእግዚአብሔርን ቅድስናና ርኅራኄ በሚወክለው መሠዊያ ላይ ነበር:: እነዚህ ሥርዐቶች ሁሉ ሕዝቡን በሚያስተምሩ፣ ሥርዐቱን በጥንቃቄና በንጽሕና ሕይወት በሚጠ ብቁ ካህናት ኀላፊነት ይከናወናሉ:: እያንዳንዱ መሥዋዕት ለእስራኤል ሕዝብ ትርጒም ያለው ቢሆ ንም መንፈሳዊና ምሳሌያዊ ትርጓሜም ነበረው::

ስለ መሥዋዕት አጠቃላይ ትርጒም በ"ሥርየት ቀን" ስለሚካሄደው (ም 16)፣ ስለ ደም ምትክ ሆኖ መሥዋዕት 17፥11፤ ዘፍ 9፥4 እና ስለሚቀርብ መሥዋዕት 16፥21 ይመ:: አንዳንድ ሰዎች በብሉይ ኪዳን ይደረጉ ስለ ነበሩት መሥዋዕቶች፣ ሰው ካለው ሀብት ለአምላኩ የሚያቀርበው የፍቅር ስጦታ እንደሆነ ይናገራሉ:: ነገር ግን የብሉይ ኪዳን መሥዋዕቶች በእግዚአብሔር የተደነገጉና እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር ካደረገው ኪዳን ጋር የተያያዘ ትርጒም ያላቸው ናቸው:: በእርግጥ የመስጠትን ሐሳብ የያዙ ቢሆኑም በዋነኛነት ግን ከመስጠት፣ ከኅብረት፣ ከኀጢአት ይቅርታና ከመመለስ ጋር የተቈራኙ ናቸው:: የተለያዩ መሥዋዕቶች የተለያዩ ዐላማዎች ቢኖራቸውም ቀዳሚ ዐላማቸው ግን የኀጢአት ስርየትና አምልኮ ናቸው (ዘፀ 25፥17 ማብ ይመ)::

### አስተዋፅኦ

1. አምስቱ ዋና ዋና መሥዋዕቶች (ም 1-7)
   ሀ. ይዘታቸው፣ ዐላማቸውና አቀራረባቸው (1፥1-6፥7)
   ለ. ተጨማሪ መመሪያዎች (6፥8-7፥38)
2. የአሮንና የልጆቹ የክህነት ሹመትና ሥራ (ም 8-10)
3. ስለ ምግብ፣ ልጅ ስለ መውለድ፣ ስለመርከስ ወዘተ የተሰጠ የመንጻት ሥርዓቶች (ም 11-15)
4. የሥርየት ቀንና በመገናኛው ድንኳን የሚደረግ አምልኮ (ም 16-17)
5. ዝሙትን፣ ታማኝነትን ማጉደል፣ ስርቆትን፣ አምልኮተ ጣኦትንና የመሳሰሉትን የሚመለከት ሕግ (ም 24፥10-23)
6. ለካህናት፣ ስለ መስዋዕቶችና ስለ ዓመት በዓላት የተሰጡ መመሪያዎች (21፥1-24፥9)

7. እግዚአብሔርን ለሰደበ፣ ነፍስ ላጠፋና ለመሳሰሉት የሚደረግ ቅጣት (24፥10-23)
8. ሰባተኛው ዓመት፣ ኢዮቤልዩ፣ የመሬት ይዞታና ከባርነት ነጻ ስለ መሆን (ም 25)
9. ኪዳኑን በመጠበቅ ወይም ባለመጠበቅ የሚመጣ በረከትና መርገም (ም 26)
10. ለእግዚአብሔር ስለሚቀርብ የስለት መሥዋዕት የተሰጠ መመሪያ (ም 27)

## የሚቃጠል መሥዋዕት

**1** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ጠራው፤ ከመገናኛውም ድንኳን እንዲህ ሲል ተናገረው፤ [2]"እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ ከእናንተ ማንም ሰው ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ከእንስሳ ወገን መባ በሚያቀርብበት ጊዜ ከላሙ፣ ከበጉ፣ ወይም ከፍየሉ መንጋ መካከል ያቅርብ::

[3]" 'መባው በሚቃጠል መሥዋዕትነት ከላሞች መንጋ መካከል የሚቀርብ ከሆነ፣ እንከን የሌለበትን ተባዕቱን መሥዋዕት በእግዚአብሔር (ያህዌ) ዘንድ ተቀባይነት እንዲያገኝ በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ ያቅርበው:: [4]የሚቃጠል መሥዋዕት ሆኖ በሚቀርበው እንስሳ ራስ ላይም እጁን ይጫን፤ ይህም ያስተሰርይለት ዘንድ በምትኩ ተቀባይነት ያገኛል:: [5]ወይፈኑን በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ይረደው፤ ካህናቱ የአሮን ልጆችም ደሙን አምጥተው በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ባለው በመሠዊያው ዙሪያ ሁሉ ይርጩት:: [6]እርሱም የሚቃጠለውን መሥዋዕት ቈዳ ይግፈፍ፤ ብልቱንም ያውጣው:: [7]የካህኑ የአሮን ልጆች በመሠዊያው ላይ ዕንጨት ረብርበው እሳት ያንድዱበት:: [8]ካህናቱ የአሮን ልጆች ጭንቅላቱንና ሥቡን ጨምረው ብልቶቹን በመሠዊያው ላይ በሚነደው ዕንጨት ላይ ይደርድሩት፤ [9]አቅራቢው የሆድ ዕቃውንና እግሮቹን በውሃ ይጠብ፤ ካህኑም መባውን ሁሉ በመሠዊያው ላይ ያቃጥል፤ ይህም በእሳት የሚቀርብ፣ ሽታውም እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ የሚቃጠል መሥዋዕት ይሆናል::

[10]" 'መባው በሚቃጠል መሥዋዕትነት ከበግ ወይም ከፍየል መንጋ መካከል የሚቀርብ ከሆነ፣ እንከን የሌለበትን ተባዕቱን ያቅርብ:: [11]የሚቀርበውን መሥዋዕት ከመሠዊያው በስተ ሰሜን በኩል በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ይረደው፤ ካህናቱ የአሮን ልጆችም ደሙን በመሠዊያው ላይ ዙሪያውን ሁሉ ይርጩት:: [12]አቅራቢው ብልቶቹን ያውጣ፤ ካህኑም ጭንቅላቱንና ሥቡን ጨምሮ በመሠዊያው ላይ በሚነደው ዕንጨት ላይ ይደርድ

1፥1 ዘፀ3፥4፤25፥22፤27፥21፤40፥2
1፥2 ዘሌ7፥16:38፤22፥21፤23፥38፤27፥9፤22፥18-19፤ዘኍ15፥3
1፥3 ቍ5:10፤ዘፍ8፥20፤ዘፀ12፥5፤ዘሌ6፥25፤17፥9፤22፥19:20:27፤ዘኍ6፥16፤ዘዳ12፥5-6:11፤ዕዝ8፥35፤ኢሳ58፥5፤ሚል1፥8፤ዕብ9፥14፤1ጴጥ1፥19
1፥4 ቍ3፤ዘፍ32፥20፤ዘፀ29፥10:15:36፤32፥30፤ዘሌ4፥29፤6፥25፤ሕዝ45፥15፤
1፥5 ቍ3፤ዘፀ29፥1:11:20፤ዘሌ3፥2:8፤8፥2፤10፥6፤21፥1፤ዘኍ15፥8፤ዘዳ18፥3፤መዝ50፥9፤69፥31፤ዕብ12፥24፤1ጴጥ1፥2
1፥6 ዘፀ29፥17፤ዘሌ7፥8፤
1፥7 ቍ17፤ዘፍ22፥9፤ዘሌ3፥5፤6፥12
1፥8 ቍ12፤ዘፀ29፥13፤ዘሌ8፥20፤9፥13 1፥9 ቍ3:13፤ዘፍ8፥21፤ዘፀ29፥17:18፤ዘሌ2፥2፤3፥5:16፤6፥22፤9፥14፤17፥6፤23፥8:25:36፤ዘኍ18፥17፤8፥6:11-13:19፤ኤፌ5፥2 1፥10 ቍ3፤ዘፍ22፥7፤ዘፀ12፥5፤ዘሌ3፥12፤4፥23:28፤5፥6፤ዘኍ15፥11 1፥11 ዘፀ29፥11:20
1፥12 ቍ8

*1፥1* ይህ ቍጥርና የመጽሐፉ መጨረሻ (27፥34) በግልጽ እንደሚያመለክቱት በኦሪት ዘሌዋውያን ውስጥ የተካተቱት (ሥርዐቶች፣ ሕጎችና ትእዛዞች) ለሙሴ የተሰጡት በእግዚአብሔር ነው:: በዚህ መጽሐፍ ውስጥ፣ "እግዚአብሔር ሙሴን... ተናገረው" የሚለው ሐረግ ከ50 ጊዜ በላይ ተጠቅሶ ይገኛል:: የዘመኑ የመጽሐፍ ቅዱስ ሐያስያን እንደሚናገሩት፣ ይህ መጽሐፍ የተጻፈው አይሁድ በምርኮ ላይ ሳሉ ወይም ከምርኮ በኋላ ሕግ የማውጣት ሥልጣን በነበራቸው ካህናት ነው:: ይሁን እንጂ ይህ አባባል ተጨባጭ ማስረጃ የሌለው፣ መጽሐፉ ራሱ በሙሴ እንደተጻፈ በተደጋጋሚ የሚያወሳውን፣ እንዲሁም ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን የአይሁድ ትውፊትና ሌሎች የብሉይና የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት የሚሰጡትን ምስክርነት የሚቃረን ነው (ሮሜ 10፥5):: በኦሪት ዘሌዋውያን ውስጥ ተጠቅሰው የሚገኙት ሐሳቦች ተጽፈዋል ተብሎ የሚታሰበው፣ በ2000 ዓ.ቅ.ክ ገደማ ሲሆን፣ ይህ ዘመን ደግሞ ሙሴ አምስቱን የኦሪት መጻሕፍት የጻፈበት ዘመን ሳይሆን አይቀርም (በኦሪት ዘፍጥረት መግቢያ ላይ፣ "ጸሓፊውና የተጻፈበት ዘመን" በሚል ርእስ ሥር የቀረበውን ይመ:: ስለ ሙሴና ስለ ሥራው የተጠቀሱ ብዙ ነገሮችን እንዳሉ እንዳንቀበል የሚያደርገን በቂ ምክንያት የለም:: *ከመገናኛው ድንኳን፤* እግዚአብሔር ከሕዝበ እስራኤል ጋር የሚገናኝበት ማደሪያ ድንኳን ማለት ነው (የዘጸ 27፥32 ማብ ይመ)::

1፥2 *መባ በሚያቀርብበት ጊዜ፤* በዚህ ቦታ፣ "መባ" ለሚለው ቃል የገባው የዕብራይስጡ ቃል "አቅርቡ" ወይም፣ "አምጡ" ተብሎ ሊተረጐም ከሚችል ቃል የተገኘ ነው:: "መባ"፣ አንድ ሰው ለእግዚአብሔር እንደ ስጦታ አድርጎ፣ "የሚያቀርበው" ወይም፣ "የሚያመጣው ነው:: (ለእግዚአብሔር የሚቀርቡ ስጦታዎች ሁሉ በፈቃድ የሚሰጡ ናቸው፤ ለምሳሌ የሚቃጠል መሥዋዕት):: ቍርባን ሌላው የመባ ስም ሲሆን ቃሉ በማርቆስም 7፥11 ላይ ተጠቅሶአል፤ ማርቆስ "ስጦታ" ብሎ ተርጕሞታል (ማብ ይመ)::

1፥3 *በሚቃጠል መሥዋዕትነት፤* የሚቃጠል መሥዋዕትን አስመልክቶ ለካህናት የተሰጠውን ተጨማሪ መመሪያ በ6፥8-13 ላይ ይመ:: የሚቃጠል መሥዋዕት ጠዋትና ማታ የሚቀርበው ለእስራኤል ሁሉ ነው (ዘጸ 29፥39-42):: በሰንበት ዕለት እጥፍ የሚቃጠል መሥዋዕት (ዘኍ 28፥9-10)፣ በበዓላት ቀኖች ደግሞ ተጨማሪ የሚቃጠሉ መሥዋዕቶች ይቀርቡ ነበር (ዘኍ 28-29):: ከዚህ በተጨማሪ ማናቸውም ሰው አምልኮቱን ለእግዚአብሔር ለመስጠት ልዩ የሆነ የሚቃጠል መሥዋዕት ማቅረብ ይችል ነበር:: *ተባዕት፤* ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚቀርበው እንስሳ ተባዕት መሆን ነበረበት፤ ተባዕት እንዲቀርብ የተደረገበት ምክንያት፣ ዋጋው ከፍ ያለ ስለ ሆነና ምናልባት ደግሞ ብርታትንና የመውለድን ዐቅም በተሻለ ሁኔታ ይገልጻል ተብሎ ነው:: ለሚቃጠል መሥዋዕት እንዲቀርብ የተወሰነው መካከለኛ ገቢ ያለው በግ ወይም ፍየል፣ ለሀብታም ኮርማ፣ ለድኻ ደግሞ ርግብ ወይም ዋኖስ ነው:: *እንከን የሌለበት፤* እንስሳው ምንም ዐይነት እንከን የሌለበት መሆን አለበት (ሚክ 1፥8):: ሌሎች መሥዋዕቶች ሲቀርቡ እንደሚደረገው ሁሉ፣ መሥዋዕቱን የሚያቀርበው ሰው በእርሱና በእንስሳው መካከል ያለውን አንድነት ለመግለጽ እጆቹን በእንስሳው ራስ ላይ ይጭናል (16፥21)፤ በዚህ ዐይነት እንስሳው በሰውየው ምትክ፣ "ያስተሰርይለት ዘንድ ... ተቀባይነት ያገኛል" (ቍ 4):: የእንስሳው ደም በትልቁ መሠዊያ ጐኖች ላይ ይረጫል (መሠዊያው የሚገኘው በኋላ ቤተ መቅደስ ከተባለው፣ ከመገናኛው ድንኳን ውጪ በስተ ምሥራቅ ባለው አደባባይ መካከል ነው)፤ የመሠዊያው እሳት ምንጊዜም አይጠፋም (6፥13) የእንስሳ ራሱን፣ እግሮቹን፣ ሥቡንና ሆድ ዕቃውን ጨምሮ መሥዋዕቱ በሙሉ መቃጠል አለበት (ቍ 9):: ለመሥዋዕት የሚቀርበው እንስሳ ኮርማ ከሆነ፣ ሥርዐቱን የሚፈጽመው ካህን ቈዳውን ይወስዳል (7፥8):: ይህ የሚቃጠል መሥዋዕት የእስራኤል አባቶች ያቀርቡት የነበረው መሥዋዕት ሳይሆን አይቀርም:: እንዲህ ያለው መሥዋዕት ሰፊ ትርጕም ያለውና ብዙ ነገሮችን የሚያካትት ነው:: የዕብራይስጡ፣ "ወደ ላይ መውጣት" የሚል ትርጕም ያለው ሲሆን፣ ይህም ምናልባት መዐዛው እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ አምልኮና ጸሎት ወደ እርሱ ማረጉን የሚያመለክት ምሳሌ ሊሆን ይችላል (ቍ 17):: የመሥዋዕቱ ሙሉ በሙሉ መቃጠል፣ በአምልኮ ውስጥ ያለው ሰው ራሱን ለእግዚአብሔር የሰጠ መሆኑን ያመለክታል:: *በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ፤* የሚቃጠለው መሥዋዕት የሚቀርብበት መሠዊያ የሚገኝበት ቦታ ነው (ዘፀ 40፥29):: *በእግዚአብሔር ዘንድ ተቀባይነት እንዲያገኝ፤* ሮሜ 12፥1፤ ፊል 4፥18 ይመ::

1፥4 *እጁን ... ይጫን፤* የቍ 3እና የዘጻ 29፥10ን ማብ ይመ:: *ያስተሰርይለት፤* የ16፥20-22፤ 17፥11 ማብ ይመ::

1፥5 የክህነት ሥራ የሚጀመረው መሥዋዕት አቅራቢው እንስሳውን ካረደ (አንድ ንጹሕ እንስሳ በአንድ ኀጢአተኛ ሰው ምትክ መሠዋቱን ተምሳሌታዊ በሆነ መንገድ ለመግለጽ) በኋላ ብቻ ነው:: *ደሙን፤* የ17፥11 እና የዕብ 9፥18ን ማብ ይመ:: *በመሠዊያው ዙሪያ ይርጩት፤* ዘፀ 24፥6 እና የዕብ 9፥19-21 ማብ ይመ::

1፥6 *ቈዳ፤* ቈዳው ብቻ ሲቀር እንስሳው በሙሉ እንዳለ ይቃጠላል፤ ቈዳው ግን ለካህኑ ይሰጣል (7፥8)::

1፥9:13:17 *ሽታውም፤* የብሉይ ኪዳን መሥዋዕቶች የሚያመለክቱት ራሱን፣ "መልካም መዐዛ" አድርጎ ራሱን ለእግዚአብሔር ያቀረበውን ክርስቶስን ነው (ኤፌ 5፥2ን ከፊል 4፥18 ጋር ያነጻጽሩ)::

1፥11 *በስተ ሰሜን በኩል፤* የመገናኛ ድንኳኑን ንድፍ የሚያሳየውን በገጽ 124 ላይ ይመ::

ረው፤ [13]አቅራቢው የሆድ ዕቃውንና እግሮቹን በውሃ ይጠብ፤ ካህኑ መባውን ሁሉ አምጥቶ በመሠዊያው ያቃጥል፤ ይህም በእሳት የሚቀርብ፣ ሽታውም እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ የሚቃጠል መሥዋዕት ይሆናል::

[14]"'ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በሚቃጠል መሥዋዕትነት የሚቀርበው መባ ከወፎች ወገን ከሆነ፣ ዋኖስ ወይም የርግብ ጫጩት ያቅርብ:: [15]ካህኑም ወደ መሠዊያው ያምጣው፤ ራሱን ቈልምሞ ይቀንጥሰው፤ የተቈረጠውንም ራስ በመሠዊያው ላይ ያቃጥል፤ ደሙም በመሠዊያው አጠገብ ይንጠፍጠፍ፤ [16]ከሆድ ዕቃውም ጥሬ ቤቱን[u] ለይቶ ከላባዎቹ ጋር ከመሠዊያው በስተ ምሥራቅ በኩል፣ ዐመድ በሚፈስበት ስፍራ ይጣለው:: [17]በክንፎቹ በኩል ለሁለት ይሰንጥቀው፤ ነገር ግን ጨርሶ አያለያየው፤ ካህኑም በመሠዊያው ላይ በሚነደው ዕንጨት ላይ ያቃጥለው፤ ይህም በእሳት የሚቀርብ፣ ሽታውም እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ የሚቃጠል መሥዋዕት ይሆናል::"

## የእህል ቍርባን

2 "'ማንኛውም ሰው የእህል ቍርባን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በሚያቀርብበት ጊዜ፣ ዱቄቱ የላመ ይሁን፤ ዘይት ያፍስበት፤ ዕጣንም ይጨምርበት፤ [2]ወደ ካህናቱም ወደ አሮን ልጆች ያምጣው:: ካህኑ ከላመው ዱቄትና ከዘይቱ አንድ እፍኝ ሙሉ ያንሣለት፤ ዕጣኑንም ሁሉ ይውሰደው፤ ይህንም በእሳት የሚቀርብ፣ ሽታውም እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ መሥዋዕት አድርጎ ለመታሰቢያ በመሠዊያው ላይ ያቃጥለው:: [3]የተረፈውም የእህሉ ቍርባን ለአሮንና ለልጆቹ ይሰጥ፤ ይህም ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በእሳት ከሚቀርበው ቍርባን እጅግ የተቀደሰ ክፍል ነው::

[4]"'በማብሰያ ምድጃ የተጋገረ የእህል ቍርባን በምታቀርብበት ጊዜ፣ ከላመ ዱቄት ተዘጋጅቶ እርሾ ሳይገባበት በዘይት ተለውሶ የተጋገረ ኅብስት ይሁን፤ አለዚያም[a] ያለ እርሾ በስሱ ተጋግሮ ዘይት የተቀባ ቂጣ ይሁን:: [5]የእህል ቍርባንህ በምጣድ የሚጋገር ከሆነ፣ እርሾ ሳይገባበት በዘይት ከተለወሰ ከላመ ዱቄት ይዘጋጅ:: [6]ቈራርሰህ ዘይት አፍስበት፤ ይህ የእህል ቍርባን ነው:: [7]የእህል ቍርባንህ በመጥበሻ የሚበስል ከሆነ፣ ከላመ ዱቄትና ከዘይት ይዘጋጅ:: [8]በዚህ ሁኔታ የተዘጋጀውን የእህል ቍርባን ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) አምጥተህ ለካህኑ አስረክብ፤ ካህኑም ወደ መሠዊያው ይወስደዋል፤ [9]ከእህሉም ቍርባን ላይ ለመታሰቢያ የሚሆነውን ክፍል ያንሣና በእሳት የሚቃጠል፣ ሽታውም እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ መሥዋዕት አድርጎ በመሠዊያው ላይ ያቃጥለዋል:: [10]የተረፈውም ቍርባን ለአሮንና ለልጆቹ ይሰጥ፤ ይህም ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በእሳት ከሚቀርበው ቍርባን እጅግ የተቀደሰ ክፍል ነው::

[11]"'እግዚአብሔር (ያህዌ) በእሳት በምታቀርቡት ቍርባን ውስጥ እርሾ ወይም ማር ጨምራችሁ ማቃጠል ስለማይገባችሁ፣ በምታቀርቡት በማንኛውም የእህል ቍርባን እርሾ አይኑርበት:: [12]እነዚህን የበኵራት ቍርባን አድርጋችሁ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ማቅረብ ትችላላችሁ፤ ነገር ግን ሽታው ደስ የሚያሰኝ ቍርባን ሆነው በመሠዊያ ላይ ለመቃጠል አይቀርቡም:: [13]የምታቀርበውን

1፥13 ቍ9፤ ዘፀ29፥17፤ ዘሌ6፥22፤ዘዳ12፥27
1፥14 ዘፍ15፥9፤ ሉቃ2፥24
1፥15 ዘሌ5፥8፡9
1፥16 ዘሌ4፥12፤ 6፥10፤ዘኍ4፥13
1፥17 ቍ7፤ ዘፍ15፥10
2፥1 ቍ2፡15፡16፤ ዘፀ29፥2፡40፡41፤ ዘሌ5፥11፤6፥14-18፤ 7፥12፤24፥7፤ ዘኍ15፥4፤28፥5፤ ነህ13፥9፤ኢሳ43፥23
2፥2 ቍ9፡16፤ ዘሌ1፥9፤5፥11፡12፤ 6፥15፤24፥7፤ዘኍ5፥26፤18፥8፤መዝ16፥5፤73፥26፤ኢሳ1፥13፤ 53፥12፤ 5፥6፤66፥3
2፥3 ቍ10፤ ዘፀ30፥36፤ ዘሌ6፥16፤10፥2፡13
2፥4 ዘፀ29፥2፤ ዘሌ7፥9፡12፤8፥26፤ 26፥26
2፥5 ዘሌ6፥21፤ 7፥9፤ሕዝ4፥3
2፥7 ዘሌ7፥9
2፥9 ቍ2፤ዘፍ8፥21
2፥10 ቍ3፤ ዕዝ2፥63
2፥11 ዘፀ23፥18፤ ዘሌ6፥16
2፥12 ዘፀ34፥22
2፥13 ዘኍ18፥19፤ 2ዜና13፥5፤

[u]16 ለዚህ ቃል የዕብራይስጡ ትርጓሜ በእርግጠኝነት አይታወቅም::
[a]4 ወይም *እንዲሁም*

1፥14 *ከወፎች፤* የሚቀርቡ መሥዋዕቶች በሦስት እንደሚከፈሉ ተመልክቶአል (1) በሬ (ቍ 3-9)፣ 2) በግና ፍየል (ቍ 10-13) እና 3) ወፎች (ቍ 14-17):: ወፎችን መሥዋዕት አድርጎ ለማቅረብ የተፈቀደላቸው ድኾች ናቸው (5፥7፤ 12፥8፤ ሉቃ 2፥24 ይመ)::

1፥17 *ጨርሶ አያለያየው፤* የዘፍ 15፥10ን ማብ ይመ::

2፥1 *የእህል ቍርባን፤* ለካህናት የተሰጠውን ተጨማሪ መመሪያ በተመለከተ በ6፥14-23፤ 7፥9-10 ላይ ይመ:: ቍርባኑ የሚዘጋጀው ከእህል ወይም ከላመ ዱቄት ነበር፤ በገበር ምጣድ የበሰለ ቂጣ ወይም በምጣድ የተጋገረ ኅብስት መሆን አለበት:: ያለ ደም የሚዘጋጀው መሥዋዕት ይህ ብቻ ሲሆን የሚቀርበውም ከሚቃጠል መሥዋዕት (ዘኍ 28፥3-6 ይመ)፤ ከኀጢአት መሥዋዕት (ዘኍ 6፥14-15 ይመ) እንዲሁም ከኅብረት መሥዋዕት (9፥4፤ ዘኍ 6፥17 ይመ) ጋር ነው:: ለሚቃጠል መሥዋዕት ከሚቀርቡት የኮርማ፣ የአውራ በግ ወይም የበግ መሥዋዕቶች ጋር ተጨማሪ ሆኖ የሚቀርበው የእህል ቍርባን መጠን ምን ያህል እንደሆነ በዘኍ 28፥12-13 ላይ ተመልክቶአል:: አንድ ዕፍኝ ሙሉ ዱቄት ተጨማሪ ሆነው ከሚቀርቡት ሌሎች መሥዋዕቶች ጋር በመሠዊያው ላይ ይቃጠላል፤ የቀረው ግን ያለ እርሾ ይጋገርና ካህናት ከተቀደሰው ምግባቸው ጋር ይበሉታል (6፥14-17):: ዱቄቱ በመሠዊያው ላይ ባጭር ጊዜ እንዲቃጠል በወይራ ዘይት ይለወሳል፤ ጣዕሙ እንዲጣፍጥ ጨው ይጨመርበታል፤ ዕጣን ይነሰነስበታል፤ ነገር ግን እርሾም ሆነ ማር ፈጽሞ አይጨመርበትም፤ እርሾና ማር በመሠዊያው ላይ መቃጠል የለባቸውምና (ቍ 11-13):: አምልኮት እየፈጸመ ያለ ሰው ከእህል ቍርባኑ አንዳችም መብላት አይገባውም፤ ካህናቱም ሙሉ በሙሉ መቃጠል ካለበት የእህል ቍርባናቸው አንዳችም መብላት የለባቸውም (6፥22-23):: የእህል ቍርባን ለሚለው ሐረግ የተተካው የዕብራይስጥ ቃል "መባ" ወይም "ስጦታ" የሚል ትርጒም ስላለው፣ አብዛኛውን ጊዜ በዚህ መልክ ገብቶ ይታያል (ዘፍ 43፥11 ይመ):: የተቀደሱ ስጦታዎች ራስን ለእግዚአብሔር አሳልፎ መስጠትን ያመለክታሉ (ቍ 2):: *ዱቄት የላመ፤* ድቅቅ ብሎ የተፈጨና በወንፊት የተነፋ ነው:: *ዘይት፤* አብዛኛውን ጊዜ የወይራ ዘይት ገና ከተሰበሰቡ ምርቶች፣ ማለትም ከእህልና ከአዲስ የወይን ጠጅ ጋር ተያይዞ ይጠቀሳል (ዘዳ 7፥13 ይመ):: የወይራ ዘይት በአብዛኛው ጥቅም ላይ የሚውለው የእህል ቍርባንን ለማዘጋጀት ሲሆን፣ ለአምልኮ የሚሄድ ሰው የሚሰጠው ተፈላጊ ስጦታ ነው:: *ዕጣን፤* በእህል ቍርባን ውስጥ የሚጨመር ዋና ቅመም ነው (ዘፀ 30፥34-35 ይመ)::

2፥3 *እጅግ የተቀደሰ ክፍል፤* ከዚህ የተነሣ በቤተ መቅደሱ ውስጥ ሆነው የሚበሉት ካህናት ናቸው ቤተሰቦቻቸው ግን እንዲበሉ አልተፈቀደላቸውም (6፥16-18)::

2፥4 *ያለ እርሾ፤* የዘጸ 12፥8፤15ን ማብ ይመ::

2፥5 *በምጣድ፤* ከሸክላ የተሠራ፣ ጒልቻ ላይ ተጥዶ ከሥሩ እሳት ሲነድድበት የሚግል ማብሰያ:: ከጊዜ በኋላ የብረት ምጣዶችም ተሠርተው ለዚህ ተግባር ውለዋል::

2፥11 *ማር፤* ምናልባት በሚያሰክር መጠጥ ውስጥ ስለሚገባ (መጠጡ እንዲፈላ ለማድረግ) በመሠዊያው ላይ እንዳይቀርብ ተከልክሎአል፤ አንዳንዶች የተከለከለበትን ምክንያት ሲናገሩ ከነዓናውያን የባዕድ አምልኮ ሥርዐታቸውን በሚፈጽሙበት ጊዜ የሚጠቀሙበት ስለሆነ ነው ይላሉ::

2፥12 *የበኵራት፤* 23፥10-11፤ ዘፀ 23፥16፡19፤ ዘኍ 15፥18-20፤ ዘዳ 18፥4-5፤26፥1-11 ይመ::

ክፍሉ የሚናገረው ስለ አረማዊው መተተኛ ስለ በለዓም ነው። ሕዝቡ ታማኝ ባይሆንም እግዚአብሔር ግን ለሕዝቡ ታማኝ ነበር፤ ምሕረቱንና ቸርነቱን በግልጽ ያሳያቸው ነበር። በለዓም በምድር ሁሉ የታወቀ ነቢይ ሲሆን፣ የእስራኤል አምላክ ያህዌ እንደ ሌሎች አማልክት በጥንቈላና በአስማት የሚሠራ መስሎት ነበር። ሆኖም በለዓም ከእውነተኛው አምላክ ጋር ፊት ለፊት ከተገናኘ በኋላ (ም22)፣ እውነተኛው አምላክ ከዚህ በፊት ከሚያውቃቸው አማልክት ሁሉ ፍጹም የተለየ መሆኑን ሊረዳ ችሏል። በለዓም በሞዓብ ንጉሥ በበላቅ አነሣሽነት እስራኤልን ለመርገም ሲነሣ እንደበቱ መርገም ተሳነው። ይልቁንም እስራኤልን ባርኮ ጠላቶቿን ረገመ (ም23-24)።

በለዓም በሰባቱ ንግሮች ላይ እግዚአብሔር በታላቅ በረከቱ እስራኤልን እንደሚጐበኝ ተናግሯል (23፥20 ይመ)። ምንም እንኳ ይህን ታላቅ በረከት ለመቀበል ሕዝቡ ታማኝ ሆኖ መገኘት ቢኖርበትም፣ የኋላ ኋላ ግን ከእግዚአብሔር ባሕርይ የተነሣ በረከቱ እውን ይሆናል (23፥19 ይመ)። እንግዲህ የዘኍልቍ መጽሐፍ የእግዚአብሔር ዓላማ ቀጣይ እንደ ሆነ ያረጋግጣል ማለት ነው። እግዚአብሔር ዐመፀኛውን ሕዝቡን ቢቀጣም፣ እስራኤል የተስፋዪቱን ምድር እንድትወርስ የወሰነውን ነገር አያጥፍም። ምክንያቱም ለእስራኤል ለመስጠት ያሰበው በረከት የተመሠረተው በሉዓላዊ ፈቃዱ ላይ ነው።

ይህ መጽሐፍ ለእስራኤልና ለቤተ ክርስቲያን ትልቅ ትምህርት አለው (ከሮሜ15፥40፤ 1ቆሮ 10፥6፡11 ጋር ያነጻጽሩ)። እግዚአብሔር በእምቢተኛ ሕዝቡ ላይ ቍጣውን ይገልጣል፤ ሆኖም ጸጋውን አትረፍርፎ ስለሚሰጥ የመቤዠት ዓላማው አይታጠፍም።

## በመጽሐፉ ውስጥ የሚታዩ እክሎች

ከእስራኤል ነገዶች የተውጣጡትና ሰራዊቱን ለማደራጀት የተመለመሉት ወንዶች ቍጥር መብዛት በዘመኑ ምሁራን ዘንድ እንቆቅልሽ ሆኖአል (ለምሳሌ 1፥46፤ 26፥51 ይመ)። ይህን ያህል ሰራዊት ለማሰለፍ ጠቅላላው የእስራኤል ሕዝብ ቍጥር ከሁለት ሚሊዮን በላይ መሆን አለበት። የሰራዊቱ ብዛት ከነበሩበት ዘመንና ቦታ፣ ከበረሓው ጕዞና ከከነዓን ነዋሪዎች ቍጥር አንጻር ሲታይ እጅግ ብዙ ነው። የ3፥43 ማብ ይመ።

ለዚህ እክል ልዩ ልዩ የመፍትሔ ሐሳቦች ተሰጥተዋል። አንዳንዶች የቍጥሮቹ ልዩነት የተፈጠረው በቅጅ ጊዜ ነው ይላሉ። ሌሎች ደግሞ 'ሺህ' ለሚለው አኀዝ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በተለይ እዚህ ላይ ከቍጥር አመልካችነቱ ይልቅ ሌላ ትርጕም አለው ይላሉ። ለምሳሌ በአንዳንድ የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍሎች ላይ 'ሺህ' የሚለው አኀዝ ብዙ ሰዎችን ለመግለጽ ገብቶአል (ኢሱ 22፥14 "የቤተ ሰቡ አለቆች"፤ 1ሳሙ 23፥23 "በይሁዳ ነገዶች ሁሉ")። ሺህ የሚለውን ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ሁለት ትርጕም (ማለትም "አለቃ" ወይም "ሺህ") አለው የሚሉም አሉ (1፥20 ይመ)። ይህ እክል በበቂ ሁኔታ መልስ ባያገኝም፣ የያዕቆብ ልጆች በግብፅ መጻተኛ ሆነው ባሳለፉበት አራት መቶ ዓመታት ውስጥ እጅግ ተባዝተው እንደ ነበር መጽሐፍ ቅዱስ ይናገራል (ዘፀ1፥7-12 ይመ)። ያም ሆነ ይህ አኀዙ የሚያመለክተን እግዚአብሔር ለሕዝቡ ምን ያህል ይጠነቀቅና ይጨነቅ እንደ ነበር፣ ታምራትም እያደረገ ሕዝቡን ይንከባከብና ይመራ እንደ ነበር ነው።

## ውቅሩ

የእስራኤል ሕዝብ የሰፈረባቸውን ቦታዎች በመመርኰዝ መጽሐፉን በሦስት ዐበይት ክፍሎች መፈረጅ ይቻላል፤ እያንዳንዱም ክፍል ቀጥሎ በተመለከተው መሠረት ሦሥት ቦታ ይከፈላል:- (1) እስራኤል ከሲና ተራራ በመነሣት ወደ ተስፋዪቱ ምድር ለመጓዝ በዝግጅት ላይ ነበረች (1፥1-10፥10)፤ ከዚያም ከሲና ወደ ቃዴስ አመራች (10፥11-12፥16)፤ (2) እስራኤል በዐመፀኛነቷ ምክንያት በቃዴስ ከረመች (13፥1-20፥13)፤ ከዚያም ከቃዴስ ወደ ሞዓብ ምድር አመራች (20፥14-22፥1)፤ (3) እስራኤል የተስፋዪቱን ምድር ለመውረስ በሞዓብ ምድር ሰፈረች (22፥2-32፥42)፤ ከዚያም ልዩ ልዩ ጕዳዮችን የሚመለከቱ የመጨረሻ መመሪያ ተሰጣት (ም 33-36)።

## አስተዋፅኦ

1. እስራኤል በሲና፤ ጕዞ ወደ ተስፋዪቱ ምድር (1፥1-10፥10)
   ሀ. የሕዝብ ቈጠራ እንዲደረግ የተሰጠ ትእዛዝ (ም 1-4)
      1. ከየነገዱ ለጦርነት የተመለመሉ ወንዶች ቍጥር (ም 1)
      2. በማደሪያው ድንኳን ዙሪያ የየነገዱ አሰፋፈርና የጕዞው አሰላለፍ (ም 2)
      3. በማደሪያው ድንኳን ዙሪያ የሌዋውያኑ አሰፋፈርና የሌዋውያኑና የእስራኤል የበኵር ልጆች ቍጥር (ም 3)
      4. በማደሪያው ድንኳን እግዚአብሔርን የሚያገለግሉ የሌዋውያን ቍጥር (ም 4)
   ለ. ሕዝቡ እንዲነጻ የተሰጠ ትእዛዝ (5፥1-10፥10)
      1. በሥርዐቱ መሠረት ስለ መንጻት የተሰጠ መመሪያ (ም 5)
      2. የናዝራዊ ስእለትና የአሮን ቡራኬ (ም 6)
      3. የማደሪያው ድንኳን ሲመረቅ 12ቱ መሪዎች ያቀረቡት ስጦታ (ም 7)
      4. የመብራቶቹ መተከልና የሌዋውያኑ መቀደስ (ም 8)
      5. የፋሲካ በዓል አከባበር (9፥1-14)

6. የክብር ደመናው መውረድና የብር መለከቶች (9፥15-10፥10)

2. ከሲና ወደ ቃዴስ የተደረገ ጕዞ (10 ፥11-12፥16)
   ሀ. የጕዞው መጀመር (10 ፥11-36)
   ለ. የሐዘን ጕዞ፤ እሳትና ድርጭቶች (ም 11)
   ሐ. የማርያምና የአሮን ተቃውሞ (ም 12)
3. እስራኤል በቃዴስ፤ በዐመፅ ምክንያት ዘገዩ (13፥1-20፥13)
   ሀ. ዐሥራ ሁለቱ ሰላዮችና ስለ መልካሙ ምድር ያቀረቡት የተለያዩ አስተያየቶች (ም 13)
   ለ. ሕዝቡ እግዚአብሔር የሰጠውን ተልእኮ አለመቀበሉና መሸነፉ (ም 14)
   ሐ. ስለ ስጦታዎች፣ ስለ ሰንበትና በልብስ ጫፍ ላይ ስለሚደረግ ዘርፍ የተሰጡ ሕጎች (ም 15)
   መ. የቆሬና የተባባሪዎቹ ዐመፅ (ም 16)
   ሠ. የአሮን በትር ማቈጥቈጥ (ም 17)
   ረ. ስለ ካህናት ተግባርና ስለሚያገኙት ድጐማ (ም 18)
   ሰ. ቀይ ጊደርና የመንጻት ውሃ (ም 19)
   ሸ. የሙሴ ኀጢአት (20፥1-13)
4. ከቃዴስ ወደ ሞዓብ የተደረገ ጕዞ (20፥14-22፥1)
   ሀ. የኤዶም መገዳደር (20፥14-21)
   ለ. የአሮን መሞት (20፥22-29)
   ሐ. የዓራድ መደምሰስ (21፥1-3)
   መ. የናሱ እባብ (21፥4-9)
   ሠ. የምንጩ መዝሙር (21፥10-20)
   ረ. የሴዎንና የዐግ መሸነፍ (21፥21-35)
   ሰ. የእስራኤል ሕዝብ ወደ ሞዓብ ምድር መግባት (21፥31-22፥1)
5. እስራኤል በሞዓብ ምድር፤ የተስፋዪቱን ምድር ለመውረስ የተደረገ ዝግጅት (22፥2-32፥42)
   ሀ. የሞዓቡ ባለቅ እስራኤልን እንዲረግምለት በለዓምን መቅጠሩ (22፥2-41)
   ለ. በለዓም በተናገረው ሰባት ንግር እስራኤልን መባረኩ (ም 23-24)
   ሐ. ብዔልፌጎርና የእስራኤል ክህደት (ም 25)
   መ. የሕዝብ ቈጠራ ለሁለተኛ ጊዜ መካሄዱ (ም 26)
   ሠ. ለአዲሱ ትውልድ የተሰጠ መመሪያ (ም 27-30)
      1. ለሴቶች የተሰጠው ርስት (27፥1-11)
      2. የሙሴ ተተኪ (27፥12-23)
      3. መሥዋዕቶችን በተመለከተ የተሰጠ ትእዛዝ (28፥1-15)
      4. በዓሎችን በተመለከተ የተሰጠ ትእዛዝ (28፥16-29፥40)
      5. ስእለትን በተመለከተ የተሰጠ ትእዛዝ (ም 30)
   ረ. ከምድያማውያን ጋር የተደረገ ጦርነት (ም 31)
   ሰ. ከዮርዳኖስ ማዶ የሰፈሩ ነገዶች (ም 32)
6. ተጨማሪ ጕዳዮችን በተመለከተ (ም 33-36)
   ሀ. በየደረጃው ያለ ጕዞ (ም 33)
   ለ. የሚወርሷት ምድር (ም 34-35)
   ሐ. ለሴቶች የተሰጠው ርስት (ም 36)

## የሕዝብ ቈጠራ

**1** እስራኤላውያን ከግብፅ በወጡ በሁለተኛው ዓመት፣ በሁለተኛው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን በሲና ምድረ በዳ ሳሉ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ተናገረው፤ እንዲህም አለው፤ 2“የወንዶቹን ስም አንድ በአንድ በመዘርዘር መላውን የእስራኤል ማኅበረ ሰብ በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ቍጠሯቸው። 3በመላው እስራኤል ያሉትን ዕድሜያቸው ሃያና ከዚያም በላይ ሆኖ ለውጊያ ብቁ የሆኑትን ወንዶች ሁሉ አንተና አሮን በየምድባቸው ቍጠሯቸው። 4ከየነገዱ የአባቶች ቤት ተጠሪ የሆነ አንድ ሰው ከእናንተ ጋር ይሁን። 5የሚረዷችሁም ሰዎች ስም የሚከተለው ነው፦

“ከሮቤል የሰዲዮር ልጅ ኤሊሱር፤
6ከስምዖን የሱሪሰዳይ ልጅ ሰለሚኤል፤
7ከይሁዳ የአሚናዳብ ልጅ ነአሶን፤
8ከይሳኮር የሶገር ልጅ ናትናኤል፤
9ከዛብሎን የኬሎን ልጅ ኤልያብ፤
10ከዮሴፍ ልጆች ከኤፍሬም የዓሚሁድ ልጅ ኤሊሳማ፤
ከምናሴ የፍዳሱር ልጅ ገማልኤል
11ከብንያም የጋዴዮን ልጅ አቢዳን፤
12ከዳን የአሚሳዳይ ልጅ አኪዔዘር፤
13ከአሴር የኤክራን ልጅ ፉግኤል፤
14ከጋድ የራጉኤል ልጅ ኤሊሳፍ፤
15ከንፍታሌም የዔናን ልጅ አኪሬ።”

16እነዚህ ከማኅበረ ሰቡ የተመረጡ የየነገዱ አለቆች ሲሆኑ እነርሱም የእስራኤል ጐሣዎች መሪዎች ነበሩ።

17ሙሴና አሮን ስማቸው የተጠቀሰውን እነዚህን ሰዎች ወሰዱ፤ 18ከዚያም በሁለተኛው ወር በመጀመሪያው ቀን ማኅበረ ሰቡን በሙሉ በአንድነት ሰበሰቧቸው። የተሰበሰቡትም በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው የትውልድ ሐረጋቸውን ተናገሩ፤ 19እግዚአብሔር ሙሴን ባዘዘው መሠረት ዕድሜአቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ የሆነ ወንዶች ስማቸው አንድ በአንድ ተመዘገበ። እንዲህ አድርጎም በሲና ምድረ በዳ ቈጠራቸው።

20ከእስራኤል የበኵር ልጅ ከሮቤል ዘርያ
ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያ በላይ ሆኖ በሰራዊቱ ውስጥ ለማገልገል ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ። 21ከሮቤል ነገድ የተቈጠሩት አርባ ስድስት ሺህ አምስት መቶ ነበሩ።

22ከስምዖን ዘርያ፦
ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ። 23ከስምዖን ነገድ የተቈጠሩት አምሳ ዘጠኝ ሺህ ሦስት መቶ ነበሩ።

24ከጋድ ዘርያ፦
ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው

1፥1 ቍ18፤ዘፀ6፥14፤19፥1፤27፥21፤40፥2
1፥2 ቍ18፤ዘፀ30፥11-16፤ዘኍ3፥40
1፥3 ቍ20፤ዘፀ4፥14፤30፥14፤ዘኍ17፥3፤ኢሱ5፥4፤1ዜና5፥18
1፥4 ቍ16፤ዘፀ18፥21፤ዘሌ24፥11፤ዘኍ7፥2፤30፥1፤31፥26፤34፥18፤ዘዳ1፥15፤ኢሱ7፥1፤22፥14
1፥5 ዘፍ29፥32፤ዘኍ2፥10፤7፥30፤10፥8፤17፥2፤ራእ7፥5
1፥6 ቍ22፤ዘኍ2፥12፤7፥36፡41፤10፥19፤25፥14
1፥7 ቍ26፤ዘፍ29፥35፤ዘፀ6፥23፤ ዘኍ7፥12፤ሩት4፥20፤1ዜና2፥10፤መዝ78፥68፤ማቴ1፥4፤ሉቃ3፥32
1፥8 ዘፍ30፥18፤ዘኍ2፥5፤7፥18፤10፥15
1፥9 ቍ30፤ዘኍ2፥7፤7፥24፤10፥16
1፥10 ቍ32፤ዘኍ2፥18፤7፥48፡53፤10፥22፤ቍ34፤2፥20፤7፥54፤10፥23
1፥11 ዘኍ2፥22፤7፥60፤10፥24፤መዝ68፥27
1፥12 ቍ38፤ዘኍ2፥25፤7፥66፤10፥25
1፥13 ቍ40፤ዘኍ2፥27፤7፥72፤10፥26
1፥14 ቍ24፤ዘኍ2፥14፤7፥42፤10፥20
1፥15 ቍ42፤ዘኍ2፥29፤7፥78፤10፥27
1፥16 ቍ4፤ዘፀ18፥ 25፤ዘኍ32፥28
1፥18 ቍ1፡2፤ዘፀ30፥14፤ዕዝ2፥59፤ዕብ 7፥3 1፥19 ዘፀ30፥12፤ዘኍ26፥63፤31፥49 1፥20 ዘፍ10፥15፤29፥32፤46፥9፤ራእ7፥5 1፥21 ዘኍ26፥7 1፥22 ዘፍ29፥33፤ራእ 7፥7 1፥23 ዘኍ26፥14 1፥24 ዘፍ30፥11፤ኢሱ13፥24-28፤ራእ7፥5

1፥1 *በሁለተኛው ዓመት በሁለተኛው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን*፤ የዘኍልቍ መጽሐፍ ትረካ የሚጀምረው እስራኤላውያን ከግብፅ ከወጡ ከዐሥራ ሦስት ወራት በኋላ ነው። ከዚያ በፊት በነበረው የአንድ ዓመት ጊዜ፣ የእስራኤል ሕዝብ የኦሪትን ሕግ በመቀበልና የመገናኛውን ድንኳን በመትከል፤ በሲና ተራራ አካባቢ ቆይተዋል። ከዚህ በኋላ ግን በሥርዐት ለመጓዝ እንደ አንድ ወታደራዊ ኀይል መከማቸትና መዘጋጀት ነበረባቸው። ከዘፀአት ጀምሮ ዘመን የመቍጠር ልማድ (ለተጨማሪ ምሳሌ 1ነገ 6፥1 ይመ) ክርስቲያኖች የክርስቶስን ልደት መሠረት በማድረግ ከሚጠቀሙበት የዘመን አቈጣጠር አሠራር ጋር ተመሳሳይነት አለው። ዘፀአት፣ እግዚአብሔር ሕዝቡን ከባርነት ቀንበር ነጻ ያወጣበት ታላቅ ተግባር ነው። *በሲና ምድረ በዳ*፤ በዕብራይስጥ ቋንቋ የተለመደው የዘኍልቍ መጽሐፍ መጠሪያ፣ “በምድረ በዳ” የሚል ሲሆን፣ የመጣውም ከዚሁ መጽሐፍ መጀመሪያ፣ ከአምስተኛው ቃል ነው። በዘኍልቍ መጽሐፍ ውስጥ የምናገኘው ታሪክ በሠላሳ ስምንት ዓመት ከዘጠኝ ወይም ከዐሥር ወር ውስጥ ስለ ተከናወኑ ጕዳዮች ነው፤ ይህም እስራኤላውያን በምድረ በዳ የተንከራተቱበት ዘመን ነው። *እግዚአብሔር ሙሴን... ተናገረው*፤ በዘኍልቍ መጽሐፍ ውስጥ አጽንዖት በስፋት ከተሰጣቸው ነገሮች አንዱ እግዚአብሔር ለሙሴ፣ በሙሴም በኩል ደግሞ ለእስራኤላውያን መናገሩ ነው። ከመጽሐፉ መጀመሪያ አንሥቶ እስከ ማጠቃለያው ቃል ድረስ (36፥13) ይህ ሐሳብ በተለያዩ መንገዶች ተደጋግሞ ተጠቅሶአል። እግዚአብሔር ሙሴን የራሱ ነቢይ አድርጎ እንደ ተጠቀመበት በ12፥6-8 ተገልጾአል። በዕብራይስጥ ቋንቋ ለዚህ መጽሐፍ ከተሰጡ ስሞች አንዱ “ዋየዳበር” የሚለው የዕብራይስጡ መጽሐፍ የመ ጀመሪያው ቃል ሲሆን፣ “እግዚአብሔር ተናገረ” ማለት ነው። *በመገናኛው ድንኳን*፤ የሚተከልና የሚነሣ፣ ለእግዚአብሔር የሚሰገድበትና እግዚአብሔር የሚመለክበት፣ የሚገለጥበትም ድንኳን።

1፥2 *ቍጠሯቸው*፤ የዕብራይስጡ አገላለጽ ሙሴና አሮን አንድ ላይ ሆነው ይህን ኀላፊነት መወጣት እንዳለባቸው የሚያመለክት የብዙ ቍጥር ነው፤ (ቍ 3 ላይ፣ “አንተና አሮን” የሚለውን ይመ)፤ ነገር ግን አብዛኛው ኀላፊነት ሙሴን የሚመለከት ነበር። የቈጠራው ዋና ዐላማ ማኅበራዊና ፖለቲካዊ ጕዳዮችን ወይም የቀረጥ አከፋፈል ሰነዶችን የሚመለከት ሳይሆን፣ ወታደራዊ ተግባርን ለማከናወን ፈረቃ ወይም ተራ ለማዘጋጀት ነበር።

1፥3 *ለውጊያ ብቁ የሆኑትን*፤ ይህ ሐረግ የቈጠራው ዋና ዐላማ ወታደራዊ ግዳጅን የሚመለከት እንደ ሆነ የሚያሳይ ሲሆን፣ በም 1 ተደጋግሞ ተጠቅሶአል፤ በ26፥2 ላይም ተጠቅሶአል።

1፥4 *ከየነገዱ... አንድ ሰው*፤ ከየነገዱ የተወከለ አንዳንድ ሰው ሙሴንና አሮንን እንዲረዳ መደረጉ ቈጠራውን በሁሉም ዘንድ ሕጋዊና ተቀባይነት ያለው ያደርገዋል።

*1፥5-16*፤ በዚህ ክፍል የተዘረዘረው የእነዚህ ሰዎች ስም በም 2፤7፤10 ላይ እንደ ገና ተጠቅሶአል። የብዙዎቹ ስሞች ትርጕም የእግዚአብሔርን ስም ያዘለ ነው። ሌዊ በቈጠራው ዝርዝር ውስጥ አልተጠቀሰም (ቍ 47-53 ይመ)።

1፥19 *በሲና ምድረ በዳ ቈጠራቸው*፤ ይህ አጭር መግለጫ ሲሆን ዝርዝሩ በቍ 20-43 ላይ ይገኛል።

*1፥20-43*፤ የተደጋገመ የአሠራርን ስልት በተከተለ ሁኔታ ለእያንዳንዱ ነገድ ሁለት ሁለት ቍጥሮች ተሰጥቶታል፤ አቀራረቡም የሚከተሉትን ያካትታል፤ (1) የነገዱ ስም፤ (2) የተቈጠሩት ሰዎች ዝርዝር ሁኔታ፤ (3) እንደ ገና የነገዱ ስም፤ (4) ጠቅላላ ከነገዱ የተቈጠሩት ሰዎች ብዛት። የእያንዳንዱ ነገድ ብዛት የመጨረሻ ቍጥር ወደ መቶ ቤት ተጠጋግቶ የተጻፈ ሲሆን፣ የጋድ ነገድ ብዛት የመጨረሻው ቍጥር ግን ወደ አምሳ ቤት የተጠጋጋ ነው፤ (ቍ 25)። በምዕራፍ ሁለት ላይ የተጠቀሰውም የእያንዳንዱ ነገድ ቍጥር ከዚህ ጋር ተመሳሳይ ነው፤ በዚሁ ምዕራፍ ውስጥ በሦስት ሦስት ነገድ የተመደቡ አራት

አንድ በአንድ ተጻፈ:: [25]ከጋድ ነገድ የተቈጠሩትም አርባ አምስት ሺህ ስድስት መቶ አምሳ ነበሩ::

[26]ከይሁዳ ዝርያ:-

ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [27]ከይሁዳ ነገድ የተቈጠሩትም ሰባ አራት ሺህ ስድስት መቶ ነበሩ::

[28]ከይሳኮር ዝርያ:-

ዕድሜአቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [29]ከይሳኮር ነገድ የተቈጠሩትም አምሳ አራት ሺህ አራት መቶ ነበሩ::

[30]ከዛብሎን ዝርያ:-

ዕድሜያቸው ሃያ አመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [31]ከዛብሎን ነገድ የተቈጠሩትም አምሳ ሰባት ሺህ አራት መቶ ነበሩ::

[32]ከዮሴፍ ልጆች:-

ከኤፍሬም ዝርያ ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [33]ከኤፍሬም ነገድ የተቈጠሩትም አርባ ሺህ አምስት መቶ ነበሩ::

[34]ከምናሴ ዝርያዎች:-

ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [35]ከምናሴ ነገድ የተቈጠሩትም ሠላሳ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ነበሩ::

[36]ከብንያም ዝርያ:-

ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ፤ [37]ከብንያም ነገድ የተቈጠሩትም ሠላሳ አምስት ሺህ አራት መቶ ነበሩ::

[38]ከዳን ዝርያ:-

ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [39]ከዳን ነገድ የተቈጠሩትም ሥልሳ ሁለት ሺህ ሰባት መቶ ነበሩ::

[40]ከአሴር ዝርያ:-

ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ [41]ከአሴር ነገድ የተቈጠሩት አርባ አንድ ሺህ አምስት መቶ ነበሩ::

[42]ከንፍታሌም ዝርያ:-

ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት ወንዶች ሁሉ በየጐሣቸውና፣ በየቤተ ሰባቸው መዝገብ መሠረት ስማቸው አንድ በአንድ ተጻፈ:: [43]ከንፍታሌም ነገድ የተቈጠሩትም አምሳ ሦስት ሺህ አራት መቶ ነበሩ::

[44]በሙሴና በአሮን፣ እያንዳንዳቸውም ቤተ ሰባቸውን በወከሉት በዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል አለቆች የተቈጠሩት ወንዶች እነዚህ ናቸው:: [45]ስለዚህ እስራኤላውያን ሁሉ ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ ሆኖ በእስራኤል ሰራዊት ውስጥ ለመዋጋት ብቁ የሆኑት በየቤተ ሰባቸው ተቈጠሩ፤ [46]ጠቅላላ ቊጥራቸውም ስድስት መቶ ሦስት ሺህ አምስት መቶ አምሳ ነበር::

1፥25 ዘፍ46፥16፤ ዘኍ26፥18፤1ዜና 5፥11
1፥26 ቍ7፤ ማቴ1፥2፤ራእ7፥5
1፥27 ዘኍ26፥22
1፥28 ዘፍ30፥18፤ ራእ7፥7
1፥29 ዘፍ30፥18፤ ዘኍ26፥25
1፥30 ዘፍ30፥20፤ ራእ7፥8
1፥31 ዘኍ26፥27
1፥32 ዘፍ49፥26፤ 41፥52
1፥33 ዘኍ26፥37፤ 1ዜና7፥20
1፥34 ዘፍ41፥51፤ ራእ7፥6
1፥36 ዘፍ35፥18፤ 2ዜና17፥17ኤር32፥44፤አብ1፥19፤ራእ7፥8
1፥37 ዘኍ26፥41
1፥38 ዘፍ30፥6፤ ዘዳ33፥22
1፥39 ዘኍ26፥43
1፥40 ዘፍ30፥13፤ ዘኍ26፥44፤ራእ7፥6
1፥41 ዘኍ26፥47
1፥42 ዘፍ30፥8፤ ራእ7፥6
1፥43 ዘፀ1፥1-4፤ ዘኍ2650
1፥44 ዘኍ26፥64
1፥45 ቍ3፤ ዘኍ2፥32፤14፥29
1፥46 ዘፀ12፥37፤ 2ሳሙ24፥9

ቡድኖች ይገኛሉ:: የእያንዳንዱን ነገድ ብዛት ለመግለጽ የተጠቀሱት ቊጥሮች መጨረሻቸው በሁለት መቶና በሰባት መቶ መካከል መሆኑ፣ አንድ ልዩ ነገር ለማመልከት ነው እንጂ ብዛታቸውን አይደለም ብለው የሚያምኑ ሰዎች አሉ:: "ለሺህ" ቊጥር የቆመውን የዕብራይስጡን ቃል ትርጒም በተመለከተም የተለያዩ ሐሳቦች ተሰንዝረዋል:: በዚህ ምዕራፍ ግን ቃሉ የገባው አጠቃላይ የቈጠራውን ድምር ለማሳየት ነው::

*1፥32-35፤* ከሌዊ ነገድ የሆኑ በቈጠራው ውስጥ ባለመግባታቸው (የቍ 47 ማብ ይመ) የዮሴፍ ዝርያ የሆኑት በሁለት ልጆቹ በኤፍሬምና (ቍ 32-33) በምናሴ (ቍ 34-35) ቤተ ሰብ መሠረት ዝርዝራቸው ተመዝግቦአል:: በዚህ ሁኔታ የዐሥራ ሁለቱ ነገድ ቊጥር ተጠብቆ ቆይቶአል፤ በውርሱም ውስጥ የሴፍ "ዕጥፍ ድርሻ" ተሰጥቶታል፤ (ከዘፍ 49፥22-26፤ ከዘዳ 33፥13-17፤ ከ2ነገ 2፥9 ጋር ያነጻጽሩ)::

1፥46 *ስድስት መቶ ሦስት ሺህ አምስት መቶ አምሳ፤* ከኢያሱና ከካሌብ በስተቀር እነዚህ ሁሉ በምድረ በዳ ሞተዋል፤ የእነዚህ ቊጥሮች ስሌት ትክክለኛነትና ውስብስብነትም አለው:: ውስብስብነቱ፣ ጠቅላላ ድምሩን በሁለት መንገድ ማግኘት ስለሚቻል ነው:- (1) የዐሥራ ሁለቱን ነገድ ቊጥር አንድ በአንድ ማስቀመጥ (ቍ 20-43)፤ ከዚያ በኋላ ጠቅላላ ድምሩን ማስፈር (ቍ 46)፤ (2) ጠቅላላውን ሕዝብ በሦስት ሦስት ነገድ አራት ቦታ በመመደብ የእያንዳንዱን መደብ መለስተኛ ድምር አቅርቦ ከዚያም በኋላ ጠቅላላ ድምሩን ማስቀመጥ (2፥3-32):: እዚህ ላይ የተጠቀሰው አኀዝ በዘፀ 12፥37፤ 38፥26 ላይ ከተጠቀሰው አኀዝ ጋር ይስማማል:: ይህ ለውትድርና የተመዘገበው የወንድ ብዛት የጠቅላላው ሕዝብ ቊጥር ከሁለት ሚሊዮን በላይ ሊሆን እንደሚችል ያመለክታል:: ዕብራውያን አራት መቶ ዓመት ግብፅ አገር በቆዩበት ዘመን በሚያስደንቅ ሁኔታ እንደ በዙ ዘፀ 1፥7 ያስረዳል:: ቊጥራቸው እጅግ ከመብዛቱ የተነሣ ለግብፅ ጸጥታ አሥጊ ደረጃ ላይ ደርሰው ነበር (ዘፀ 1፥9-10:20)፤ ግብፅ ከገቡ ሰባ ሰዎች (ዘፀ 1፥5) ተነሥቶ፣ የእስራኤል ሕዝብ ቊጥር በአስገራሚ ሁኔታ ይህን ያህል መብዛቱ የእግዚአብሔርን ታላቅ በረከትና ከአብርሃም ጋር ለገባው ኪዳኑ (ዘፍ 12፥2፤ 15፥5፤ 17፥4-6፤ 22፥17) ታማኝ መሆኑን ያሳያል::

[47]የሌዊ ነገድ ቤተ ሰቦች ግን ከሌሎች ጋር አብረው አልተቈጠሩም፤ [48]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ ብሎት ነበርና፤ [49]"የሌዊን ነገድ አትቍጠር፤ በእስራኤላውያንም ቈጠራ ውስጥ አታስገባው፤ [50]በዚህ ፈንታ ሌዋውያንን በምስክሩ ማደሪያ፣ በውስጡ ባሉት በመገልገያ ዕቃዎች ሁሉ እንዲሁም ከዚሁ ጋር በተያያዙ በማናቸውም ነገሮች ላይ ኀላፊዎች ይሁኑ፤ ማደሪያውንና በውስጡ ያሉትን የመገልገያ ዕቃዎች ይሸከሙ፤ በውስጡ ያገልግሉ፤ ድንኳናቸውንም በዙሪያው ይትከሉ። [51]ማደሪያው በሚነሣበት ጊዜ ሌዋውያን ይንቀሉት፤ ማደሪያው በሚተከልበትም ጊዜ ሌዋውያን ያቁሙት፤ ሌላ ሰው ቢቀርብ ግን ይገደል። [52]እስራኤላውያን በየምድባቸው ድንኳናቸውን ይትከሉ፤ እያንዳንዱም ሰው በየሰፈሩና በየዐርማው ሥር ይስፈር። [53]ሌዋውያን ግን በእስራኤላውያን ማኅበረ ሰብ ላይ ቍጣ እንዳይወርድ ድንኳኖቻቸውን በምስክሩ ማደሪያ ዙሪያ ይትከሉ፤ የምስክሩ ማደሪያ ድንኳን ኀላፊዎች ሌዋውያን ናቸው።

[54]እስራኤላውያንም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ይህን ሁሉ አደረጉ።

1፥47 ዘኍ3፥17-20፤4፥3:49
1፥50 ዘፀ16፥34፤25፥9፤26፥1፤ዘኍ3፥31፤ሐሥ7፥21፥12፤26፥1፤ዘኍ3፥38፤4፥5:15
1፥52 ዘኍ10፥14፤መዝ20፥5፤ማሕ2፥4፤6፥4
1፥53 ዘፀ38፥21፤ዘኍ2፥10፤3፥23:29:38፤16፥46፤18፥24:5፤29:38፤ዘሌ10፥6፤ዘዳ9፥22
2፥2 መዝ74፥4፤ኢሳ31፥9፤ኤር4፥21

## የየነገዱ አሰፋፈር

**2** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [2]"እስራኤላውያን ከምስክሩ ድንኳን ትይዩ ዙሪያውን ጥቂት ራቅ ብለው እያንዳንዱ ሰው በየዐርማውና በየቤተ ሰቡ ምልክት ሥር ይስፈር።"

*1፥47፤* ሌዋውያን የተለየ ተግባር ስለ ነበራቸው በዚህ ወታደራዊ ቈጠራ ውስጥ አልገቡም። እነርሱም እግዚአብሔርን ማገልገል ይገባቸዋል፤ ይሁን እንጂ ልዩ ተግባራቸው የማደሪያውን ድንኳን የአምልኮ ሥርዐት ማስፈጸምና የድንኳኑን ሁኔታ መንከባከብ ነበር (የቍ 32-35 ማብ ይመ)።

1፥50 *በምስክሩ፤* በታቦቱ ውስጥ የሚገኙትንና (ዘፀ 25፥16:21፤ 40፥20) በድንጋይ ጽላቶች ላይ የተጻፉትን ዐሠርቱ ትእዛዛትን (ዘፀ 31፥18:18፤ 32፥15፤ 34፥29) የሚያመለክት ሲሆን፣ "የምስክሩ ታቦት" (ዘፀ 25፥22፤ 26፥33:34) የሚለው ሐረግም ከዚሁ ቃል ጋር የተያያዘ ነው።

1፥51 *ሌላ ሰው፤* ይህ ሐረግ በዕብራይስጥ፣ "እንግዳ"፣ "ባዕድ" ወይም "መጻተኛ" የሚል ትርጕም አለው (ለምሳሌ ኢሳ 1፥7፤ ሆሴ 7፥9 ይመ)። ስለዚህ ከሌዊ ነገድ ያልሆነ እስራኤላዊ በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ለሚከናወን ሃይማኖታዊ ተግባር እንደ ባዕድ ይቈጠር ነበር (ዘፀ 29፥33፤ 30፥33፤ ዘሌ 22፥12 ይመ)። *ይገደል፤* 3፥10:38፤ 18፥7 ይመ፤ ከ16፥31-33፤ 1ሳሙ 6፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥53 *ቍጣ፤* ሌዋውያን ያልሆኑ እስራኤላውያን ወደ ምስክሩ ማደሪያ በመቅረብ ኀጢአት እንዳይፈጽሙና የመለኮት ቍጣ እንዳይደርስባቸው ሌዋውያኑ በመካከል ገብተው መከላከያ ሆኑ። *ድንኳኖቻቸውን በምስክሩ ማደሪያ ዙሪያ፤* 3፥21-38 ይመ።

1፥54 *እግዚአብሔር ሙሴን ባዘዘው መሠረት፤* በዘኍልቍ መጽሐፍ በስተ መጨረሻ ባሉት ምዕራፎች ከሚታየው ከእስራኤላውያን ታላቅ አለመታዘዝ አንጻር፣ መጀመሪያ ላይ የሚያሳዩት በጎ መታዘዝ ልብ የሚነካ ነው።

*2፥1-34፤* ይህ ምዕራፍ የያዘው ሐሳብ ሚዛን በጠበቀ ሁኔታ የተዋቀረ ነው፦

- አጠቃላይ ትእዛዝ (ቍ 1-2)
  - የአፈጻጸም ዝርዝር (ቍ 3-33)
    - በምሥራቅ በኩል ያለው ሰፈር (ቍ 3-9)
    - በደቡብ በኩል ያለው ሰፈር (ቍ 10-16)
      - የመገናኛው ድንኳንና ሌዋውያን (ቍ 17)
    - በምዕራብ በኩል ያለው ሰፈር (ቍ 18-24)
    - በሰሜን በኩል ያለው ሰፈር (ቍ 25-31)
      - ጠቅላላ ብዛት (ቍ 32-33)
- አጭር መደምደሚያ (ቍ 34)

በምዕራፍ አንድ ላይ ሕዝቡ ተሰብስቦ ተመዘገበ፤ የትውልድ ሐረጉም ተገለጸ ይላል። በምዕራፍ ሁለት ላይ ደግሞ ሕዝቡ በየምድባቸው፣ በጕዞ አሰላለፋቸውና በየሰፈራቸው በመሆን በሥርዐት ተዋቀሩ ይልና በምዕራፍ አንድ ላይ የተመዘገበው ቍጥር በምዕራፍ ሁለት ላይ እንደ ገና በአዲስ አቀራረብ ተጠቅሶአል፤ የመጀመሪያ መሪዎችም ስም በድጋሚ ተገልጾአል።

2፥2 *ጥቂት ራቅ ብለው፤* 1፥52-53 ይመ። *እያንዳንዱ ሰው፤* በሰፈሩ ውስጥ እያንዳንዱ ትክክለኛ ቦታውን ለይቶ ማወቅ ነበረበት። *በየዐርማው... ምልክት፤* እያንዳንዱ ነገድ የራሱ ምልክት ነበረው፤ እያንዳንዱም ሦስትዮሽ የነገድ ምድብ የተለየ ዐርማ

## የእስራኤል ነገዶች አሰፋፈር

ዘኍ 2፡1-31፤10፡11-33



[3] "በምሥራቅ በኩል በፀሓይ መውጫ የይሁዳ ምድብ በየሰራዊቱና በዐርማቸው ሥር ይስፈር፤ የይሁዳ ሕዝብ አለቃ የአሚናዳብ ልጅ ነአሶን ነው፤ [4] የሰራዊቱም ብዛት ሰባ አራት ሺህ ስድስት መቶ ነው።

[5] "ከእነዚህ ቀጥሎ የይሳኮር ነገድ ይሰፍራል፤ የይሳኮር ሕዝብ አለቃ የሶገር ልጅ ናትናኤል ሲሆን፤ [6] የሰራዊቱም ብዛት አምሳ አራት ሺህ አራት መቶ ነው።

[7] "ከዚያም የዛብሎን ነገድ ይቀጥላል፤ የዛብሎን ሕዝብ አለቃ የኬሎን ልጅ ኤልያብ ሲሆን፣ [8] የሰራዊቱም ብዛት አምሳ ሰባት ሺህ አራት መቶ ነው።

[9] በየሰራዊታቸው ሆነው ከአይሁድ ምድብ የተመዘገቡ አንድ መቶ ሰማንያ ስድስት ሺህ አራት መቶ ናቸው፤ እነዚህ አስቀድመው ይወጣሉ።

[10] "በደቡብ በኩል የሮቤል ምድብ ሰራዊት በዐርማቸው ሥር ይሆናል፤ የሮቤል ሕዝብ አለቃ የሰዲዮር ልጅ ኤሊሱር ሲሆን፣ [11] የሰራዊቱም ብዛት አርባ ስድስት ሺህ አምስት መቶ ነው።

[12] "ከእነዚህ ቀጥሎ የስምዖን ነገድ ይሰፍራል፤ የስምዖን ሕዝብ አለቃ የሱሪሰዳይ ልጅ ሰለሚኤል ሲሆን፣ [13] የሰራዊቱም ብዛት አምሳ ዘጠኝ ሺህ ሦስት መቶ ነው።

[14] "ከዚያም የጋድ ነገድ ይቀጥላል፤ የጋድ ሕዝብ አለቃ የራጉኤል[υ] ልጅ ኤሊሳፍ ሲሆን፣ [15] የሰራዊቱም ብዛት አርባ አምስት ሺህ ስድስት መቶ አምሳ ነው።

[16] በየሰራዊታቸው ሆነው ከሮቤል ምድብ የተመዘገቡት ወንዶች በሙሉ አንድ መቶ አምሳ አንድ ሺህ አራት መቶ አምሳ ናቸው፤ እነዚህ ቀጥለው ይመጣሉ።

[17] "ከዚህ በኋላ የመገናኛው ድንኳንና የሌዋውያን ምድብ በመካከል ሆነው ይጓዛሉ፤ እያንዳንዳቸውም አሰፋፈራቸውን በመከተል ቦታቸውን ጠብቀው በዐርማቸው ሥር ይጓዛሉ።

[18] በምዕራብ በኩል የኤፍሬም ምድብ ሰራዊት በዐርማቸው ሥር ይሆናል፤ የኤፍሬም ሕዝብ አለቃ የዓሚሁድ ልጅ ኤሊሳማ ሲሆን፣ [19] የሰራዊቱም ብዛት አርባ ሺህ አምስት መቶ ነው።

[20] "ከእነዚህም የምናሴ ነገድ ይቀጥላል፣ የምናሴ ሕዝብ አለቃ የፍዳሱር ልጅ ገማልኤል ሲሆን፣ [21] የሰራዊቱም ብዛት ሠላሳ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ነው።

[22] ከዚያም የብንያም ነገድ ይቀጥላል፣ የብንያም ሕዝብ አለቃ የጋዴዮን ልጅ አቢዳን ሲሆን፣ [23] የሰራዊቱም ብዛት ሠላሳ አምስት ሺህ አራት መቶ ነው።

[24] በየሰራዊታቸው ሆነው ከኤፍሬም ምድብ የተመዘገቡት ወንዶች በሙሉ አንድ መቶ ስምንት ሺህ አንድ መቶ ናቸው፤ እነዚህ ሦስተኛ ሆነው ይመጣሉ።

[25] "በሰሜን በኩል የዳን ምድብ ሰራዊት በዐርማው ሥር ይሆናል፤ የዳን ሕዝብ አለቃ የአሚሳዳይ ልጅ አኪዔዘር ሲሆን፣ [26] የሰራዊቱም ብዛት ሥልሳ ሁለት ሺህ ሰባት መቶ ነው።

[27] "የአሴር ነገድ ከእነዚህ ቀጥሎ ይሰፍራል፤ የአሴር ሕዝብ አለቃ የኤክራን ልጅ ፋግኤል ሲሆን፣ [28] የሰራዊቱም ብዛት አርባ አንድ ሺህ አምስት መቶ ነው።

[29] ከዚያም የንፍታሌም ነገድ ይቀጥላል፤ የንፍታሌም ሕዝብ አለቃ የዔናን ልጅ አኪሬ ሲሆን፣ [30] የሰራዊቱም ብዛት አምሳ ሦስት ሺህ አራት መቶ ነው።

[31] "በየሰራዊታቸው ሆነው ከዳን ምድብ የተመዘገቡት ወንዶች ሁሉ አንድ መቶ አምሳ ሰባት ሺህ ስድስት መቶ ናቸው፤ እነርሱም በዐርማቸው ሥር በመጨረሻ ይመጣሉ።

[υ]14 ብዙ የማሶሬቲክ፣ የአራት ሳምራውያንና የቩልጌት ቅጆች ጸዑኤል ይላሉ (ዘኍ 1፥14 ይመ)፤ አያሌ የማሶሬቲክ ቅጆች ግን ከዚህ ይስማማሉ።

2፥3 ዘፀ6፥23
2፥5 ዘኍ10፥15፤ 1፥8
2፥7 ዘኍ1፥9፤ 10፥16
2፥9 ዘኍ10፥14፤ መሳ1፥1
2፥10 ዘኍ1፥5:53
2፥12 ዘኍ1፥6፤ 10፥19
2፥14 ዘኍ1፥14፤ 10፥20
2፥16 ዘኍ10፥18
2፥17 ዘኍ1፥50፤ 10፥21
2፥18 ዘፍ48፥20፤ ዘኍ1፥10፤53፤ኤር 31፥18-20
2፥20 ዘፍ48፥20፤ ዘኍ1፥10
2፥22 ዘኍ1፥11፤ 10፥24
2፥24 ዘኍ10፥22፤ መዝ80፥2
2፥25 ዘኍ1፥12፤ 3፤10፥25
2፥27 ዘኍ1፥13፤ 10፥26
2፥29 ዘኍ1፥15፤ 10፥27
2፥31 ዘኍ10፥25፤ ኢሱ6፥9

ነበረው። የነገድ ምልክት (ሰንደቅ ዐላማ) ቀለም በሊቀ ካህናቱ የደረት ኪስ ላይ ከነበሩት ዐሥራ ሁለቱ የድንጋይ ፈርጦች (ዘፀ 28፥15-21) ቀለም ጋር እንደሚመሳሰል የአይሁድ ወግ ያወሳል። በይሁዳ የሚመራው ሦስትዮሽ የነገድ ምድብ ዐርማው የአንበሳ ምስል፣ በሮቤል የሚመራው ሦስትዮሽ ምድብ የሰው ምስል፣ በኤፍሬም የሚመራው ምድብ የበሬ ምስል፣ በዳን የሚመራው ምድብ ደግሞ የንስር ምስል እንደ ነበረባቸው በዘልማድ ይነገራል፤ (በሕዝ 1፥10 ላይ የተገለጹትን አራቱን እንስሳት ይመ፤ ከራእ 4፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። ሆኖም ይህ አባባል በትውፊት ከመነገሩ ውጭ ሌላ ተጨባጭ ማስረጃ የለውም።

2፥3-7 *ይሁዳ ... ይሳኮር ... ዛብሎን*፤ የያዕቆብና የልያ አራተኛ፣ አምስተኛና ስድስተኛ ልጆች ናቸው። ሮቤል የያዕቆብ የበኵር ልጅ መሆኑ እየታወቀ (1፥20) በአሰላለፍ ቅደም ተከተል እነዚህ ነገዶች የመጀመሪያ መሆናቸው የሚያስደንቅ ነው። ታላላቅ ወንድሞቹ ሮቤል፣ ስምዖንና ሌዊ ሆነው ባለመገኘታቸው (ዘፍ 49፥3-7 ይመ) ይሁዳ በወንድሞቹ መካከል የክብር ስፍራ ተሰጥቶታል (ዘፍ 49፥8)። መሲሑ የመጣበት ንጉሣዊ የትውልድ ሐረግ የተገኘው ከይሁዳ ነው (ዘፍ 49፥10፤ ሩት 4፥18-21፤ ማቴ 1፥1-16)።

2፥10-12 *ሮቤል ... ስምዖን*፤ የያዕቆብና የልያ የመጀመሪያና ሁለተኛ ልጆች ናቸው።

2፥14 *ጋድ*፤ ያዕቆብ የልያ ገረድ ከነበረችው ከዘለፋ የወለደው የመጀመሪያ ልጅ ነው። የልያ ሦስተኛው ልጅ ሌዊ በሕዝብ ቈጠራና ምደባ ውስጥ አልገባም።

2፥17 *የመገናኛው ድንኳን*፤ እግዚአብሔር በሰፈሩ መካከል መገኘቱን ይገልጻል፤ (1፥1 እና ማብ ይመ)። *ሌዋውያን*፤ በጕዞ አሰላለፍ፥ የይሁዳና የሮቤል ምድብ ኅብረተ ሰቡን ይመራል፤ የማደሪያው ድንኳንም እንደ ዐጥር በከለሉት ሌዋውያን በመታጀብ ቀጥሎ ይሄዳል፤ (የ1፥53 ማብ ይመ)፤ በመጨረሻም በኤፍሬምና በዳን የሚመራው ምድብ ይመጣል።

*2፥18-22*፤ በምዕራብ በኩል የራሔል ነገዶች (ዮሴፍና ብንያም) ሰፍረው ነበር። የዮሴፍ ሁለት ልጆች ምናሴና ኤፍሬም ከአያታቸው ከያዕቆብ ልዩ ምርቃት ተቀብለዋል፤ ነገር ግን ታናሽየው ኤፍሬም በምናሴ ላይ የበላይነት ተሰጥቶታል (ዘፍ 48፥5-20)። በዚህም ክፍል ያዕቆብ እንደ ተናገረው ኤፍሬም ከምናሴ ይልቅ ቀዳሚ ሆኖ ይገኛል። መጨረሻ ላይ የተሰለፈው ብንያም የያዕቆብ ልጆች ሁሉ ታናሽ ነው።

2፥25 *ዳን*፤ የራሔል ገረድ የነበረችው የባላ የመጀመሪያ ልጅ ነው።

2፥27 *አሴር*፤ የራሔል ገረድ የነበረችው የዘለፋ ሁለተኛ ልጅ ነው።

2፥29 *ንፍታሌም*፤ የባላ ሁለተኛ ልጅ ነው።

[32]በየቤተ ሰባቸው፣ በየምድባቸውና በየሰራዊታቸው የተመዘገቡት እስራኤላውያን ስድስት መቶ ሦስት ሺህ አምስት መቶ አምሳ ናቸው፤ [33]ያም ሆኖ ግን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ሌዋውያኑ ከሌሎቹ እስራኤላውያን ጋር አልተቈጠሩም።

[34]ስለዚህ እስራኤላውያን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን ያዘዘውን ሁሉ አደረጉ፤ በየአርማውም ሥር የሰፈሩትና፣ እያንዳንዳቸው በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው የተጓዙት በዚህ ሁኔታ ነበር።

**ሌዋውያን**

**3** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን በሲና ተራራ ላይ ባነጋገረው ጊዜ የአሮንና የሙሴ ትውልድ ይህ ነበር፤ [2]የአሮን ልጆች የበኵሩ ስም ናዳብ፣ የሌሎቹም አብዩድ አልዓዛርና ኢታምር ይባላል። [3]እርሱ ለክህነት አገልግሎት የለያቸው፣ ካህናት ለመሆን የተቀቡት የአሮን ወንድ ልጆች ስም ይህ ነው፤ [4]ናዳብና አብዩድ ግን በሲና ምድረ በዳ ባልተፈቀደ እሳት *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) *መሥዋዕት* ባቀረቡ ጊዜ እዚያው እፊቱ ወድቀው ሞቱ። ወንዶች ልጆች ስላልነበሩአቸውም አልዓዛርና ኢታምር ብቻ አባታቸው አሮን በሕይወት በነበረበት ዘመን በክህነት ያገለግሉ ነበር።

[5]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [6]“የሌዊን ነገድ አምጥተህ ካህኑን አሮንን በአገልግሎቱ እንዲረዱት ከፊቱ አቁማቸው፤ [7]በመገናኛው ድንኳን የማደሪያውን አገልግሎት በመፈጸም ለእርሱና ለማኅበረ ሰቡ ሁሉ የሚያስፈልጉትን ተግባሮች ያከናውኑ፤ [8]የማደሪያውን ሥራ በመሥራትና የእስራኤላውያንን ግዴታ በመወጣት የመገናኛውን ድንኳን ሁሉ ይጠብቁ። [9]ሌዋውያኑን ለአሮንና ለልጆቹ ስጥ፤ እነርሱም ከእስራኤላውያን ተለይተው ለእርሱ[a] ፈጽመው የተሰጡ ናቸው። [10]አሮንንና ልጆቹን ሹማቸው፤ እነርሱም ክህነታቸውን ይጠብቁ፤ ሌላ ሰው ማደሪያውን ቢቀርብ ግን ይገደል።”

[11]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [12]“እነሆ፤ በኵር ሆኖ በሚወለደው ሁሉ ምትክ ሌዋውያኑን ከእስራኤላውያን ወስጃለሁ፤ ስለዚህ ሌዋውያን የእኔ ናቸው፤ [13]በኵር የሆነ ሁሉ የእኔ ነውና። በግብፅ ምድር በኵር የሆነውን ሁሉ በመታሁ ዕለት ከሰውም ሆነ ከእንስሳ ማናቸውንም የእስራኤልን በኵር ለራሴ ለይቻለሁ፤ የእኔ ይሁን። እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነኝ።”

[14]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን በሲና ምድረ በዳ፣ [15]“ሌዋውያንን በየቤታቸውና በየጐሣቸው ቍጠር፤ የምትቈጥረውም አንድ ወርና ከዚያ በላይ የሆነውን ወንድ ሁሉ ነው” አለው።

2፥32 ዘኍ1፥45፤ ዘፀ12፥37
2፥33 ዘኍ1፥47፤ 26፥57-62
3፥1 ዘፀ6፥27፤ 19፥11
3፥2፤ ዘፀ6፥23፤ ዘኍ1፥20
3፥3 ዘፀ28፥41፤ 29፥30
3፥4 ዘሌ10፥1:2: 6:12፤ዘኍ4፥28፤ 1ዜና24፥1
3፥6 ዘኍ8፥6-22፤ 18፥1-7፤ዘዳ10፥8፤ 31፥9፤1ዜና15፥2፤ 2ዜና29፥11
3፥7 ዘኍ1፥53፤ 8፥19፤ዘሌ8፥35
3፥9 ቍ12:45፤ ዘኍ8፥19፤18፥6
3፥10 ዘፀ29፥9፤ 30፥7፤ዘኍ1፥51
3፥12 ቍ9:41፤ዘፀ 13፥2፤ዘኍ8፥14:16: 18፥16፤ነህ13፥29፤ ሚል2፥4
3፥13 ዘፀ13፥12፤ ዘሌ11፥44
3፥14 ዘፀ19፥1
3፥15 ቍ22፤39፤ ዘኍ1፥19፤18፥16፤ 26፥62

[a]9 ብዙ የማሶሬቲክ ቅጆች ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ ጥቂት የማሶሬቲክ፣ የኦሪተ ሳምራውያንና የሰባ ሊቃናት ቅጆች ግን ለእኔ ይላሉ።

2፥32 *ስድስት መቶ ሦስት ሺህ አምስት መቶ አምሳ፤* 1፥46 እና ማብ ይመ።

2፥33 *ሌዋውያን፤* የ1፥47-53 ማብ ይመ።

2፥34 *እግዚአብሔር ሙሴን ያዘዘውን ሁሉ አደረጉ፤* በ1፥54 ላይ እንደ ተጠቀሰው ይህ ሐሳብ በፍጹም መታዘዝን የሚያመለክት ሲሆን፣ ወደ ኋላ ከሚከሠተው የእስራኤል አለመታዘዝ ጋር በማገናዘብ የሚታይ ነው። በየዐርማው፣ በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ቍጥራቸው እጅግ ብዙ የሆነ ከባርነት በቅርብ ነጻ የወጣንና ሥርዐት ያልያዘን ሕዝብ በዚህ መልክ ማደራጀት ትልቅ ክንዋኔ ነው። በለዓም፣ “ያዕቆብ ሆይ፤ ድንኳኖችህ፣ እስራኤል ሆይ፤ ማደሪያዎችህ እንዴት ያማሩ ናቸው”(24፥5) ያለው የሕዝቡ አሰፋፈር ሥርዐት የተጠበቀ ከመሆኑ የተነሣ ሊሆን ይችላል።

3፥1 *የአሮንና የሙሴ፤* በመጀመሪያ እይታ የስሞቹ አቀማመጥ ቅደም ተከተልን ያልጠበቀ ይመስላል፤ ነገር ግን ገለጻው በአሮን ቤተ ሰብ ላይ የሚያተኵር ስለ ሆነ (ቍ 2 ይመ) ለግንዛቤ እንደዚህ መጻፉ ትክክል ነው።

3፥3 *ካህናት ለመሆን የተቀቡት፤* በክህነት ጌታን እንዲያገለግሉ ሙሴ ወንድሙን አሮንንና ወንዶች ልጆቹን እንዲቀባቸው እግዚአብሔር እንዳዘዘው ዘፀ 28፥41 ላይ ተመዝግቦ ይገኛል፤ (ዘፀ 30፥30፤ ዘሌ 8፥30 ይመ)። በዚህ ክቡር ሥርዐት መሠረት በተለየ መንገድ ለጌታ ይቀደሳሉ። ነገሥታትም (1ሳሙ 16፥13) በተለየ መንገድ እግዚአብሔርን እንዲያገለግሉ በዘይት ይቀቡ ነበር። ግዑዛን ነገሮችም ይቀቡ ነበር (ዘፍ 28፥18፤ ዘፀ 29፥36 ይመ)። በዕብራይስጡ “የተቀባ” የሚለው ቃል ከጊዜ በኋላ በተለይ መሲሑን (ክርስቶስን) ለማመልከት ውሎአል። *የተቀቡት፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጥ ቃል በቀሙ “የ... እጅ መሙላት” ማለት ነው (ዘፀ 32፥29 ይመ)፤ በዚህ ሥርዐት ውስጥ ሥልጣን መስጠት፣ መቀደስንና መለየት ያካትታል።

3፥4 *ናዳብና አብዩድ፤* ዘሌ 10፥1-3 እና ማብ ይመ። *ባልተፈቀደ እሳት፤* “ልዩ እሳት” ማለት ይቻላል፤ ተራኪው ድርጊታቸው ተገቢ አለመሆኑን ቢረዳም ሆን ብሎ ግልጽ ያልሆነ ሐረግ የተጠቀመ ይመስላል። እግዚአብሔር ያላዘዘውን እሳት ተጠቅመው ነበር (ዘሌ 10፥1)። ወደ እግዚአብሔር ቅድስና ለመቅረብ ካህናቱ የጽድቅና የመታዘዝ ሕይወት ሊኖራቸው ይገባል። አዲስ የተሾሙት የአሮን ልጆች ሞት፣ የእግዚአብሔር አገልጋዮች አገልግሎታቸው ምን ያህል ክቡርና የሚያስፈራ እንደ ሆነ ሁል ጊዜ ለማስጠንቀቅ ይጠቅማል (ከ1ሳሙ 2፥12-17:22-25: 27-36፤ 3፥11-14፤ 4፥1-11 ጋር ያነጻጽሩ)። በማዳን ታሪክ ውስጥ ገና በጅማሬው ላይ ተመሳሳይ መለኮታዊ የቅጣት ርምጃ ስለ መወሰዱ ኢሱ 7፤ 2ሳሙ 6፥7፤ ሐሥ 5፥1፥11 ይመ።

*3፥5-10፤* በምዕራፍ አንድና ሁለት ላሉት ትእዛዞች እንደ ተደረገው፣ እዚህ ላይ ለተጠቀሱት ትእዛዞች የሕዝቡን መታዘዝ በማስከተል አልተጻፈም፤ ነገር ግን በምዕራፍ ስምንት ሰፋ ያለ ተጨማሪ ገለጻ ተሰጥቶአል። በዚህ ክፍል በአሮን ልጆችና በሌዋውያን መካከል ያለው ልዩነት በግልጽ ተመልክቶአል። ሌዋውያን የተመደቡት ካህናትን ይረዱ ዘንድ ነበር፤ በዚህም አሮንን ብቻ ሳይሆን አብረው የሚጓዙትን ጠቅላላውን ሕዝብ አገልግለዋል፤ (ቍ 7-8 ይመ)።

3፥9 *ለእርሱ፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። እዚህ ላይ ሐሳቡ ለአሮን የሚደረገውን (በእርሱም በኩል ለእግዚአብሔር የሚደረገውን) አገልግሎት የሚመለከት ነው፤ በ8፥16 ላይ አገልግሎቱ በቀጥታ ለእግዚአብሔር እንደ ሆነ ተጠቅሶአል።

3፥10 *ሌላ ሰው፤* ቀጥታ ትርጕሙ፣ “እንግዳ” ማለት ሲሆን፣ ሥልጣን የሌለውና፣ ያልተፈቀደለት ለማለት ነው። በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ለማገልገል የሚቻለው እግዚአብሔር በግልጽ ሲሾም ብቻ ነው። በቍ 10 ላይ ያለው ሐሳብ የተጠቀሰው ስለ አሮን ልጆች ሞት ከሚናገረው አንቀጽ ቀጥሎ ነው። እነዚህ ሥልጣን የተሰጣቸው ሰዎች ነበሩ፤ ነገር ግን ያልተፈቀደውን ነገር አደረጉ። የአሮን ልጆች ገና ከመሾማቸው፣ መጀመሪያ ላይ በሞት ከተቀጡ፣ ያልተሾመው ሰውማ ሕግ መተላለፍ ቀርቶ እንዴት ደፍሮ ስለ መተላለፍ ሊያስብ ይችላል? ቍ 38፤ 18፥7 ይመ።

*3፥12-13፤* የዘፀ 13፥2 ማብ ይመ። *የእኔ፤* አጽንዖት ወይም ግንዛቤ ለመስጠት የተደገመ ቃል ነው።

3፥12 *ምትክ፤* አንድን ሰው በሌላው መተካት የተለመደ አሠራር ስለ መሆኑ አንድ ምሳሌ ነው (ዘፍ 22፥13 እና ማብ፤ ማቴ 20፥28 ይመ)።

3፥15 *አንድ ወርና ከዚያ በላይ፤* እዚህ ላይ ከሃያ ዓመት መሆኑ ቀርቶ ከአንድ ወር ጀምሮ ያለው ወንድ ሁሉ ይቈጠር ከማለቱ በስተቀር በሌዋውያን የተደረገው አቈጣጠር በምዕራፍ አንድና ሁለት ላይ በሌሎች ነገዶች ከተደረገው ቈጠራ ጋር

16ስለዚህ ሙሴ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ቃል በታዘዘው መሠረት እነዚህን ቈጠራቸው።

17የሌዊ ልጆች ስም
ጌድሶን፣ ቀዓትና ሜራሪ ነው።
18የጌድሶን ልጆች ጐሣ ስም
ሎቢኒና ሰሜኢ ነው።
19የቀዓት ጐሣዎች፤
እንበረም፣ ይስዓር፣ ኬብሮን፣ ዑዝኤል።
20የሜራሪ ጐሣዎች፤
ሞሖሊና ሙሲ።

እንግዲህ የሌዋውያን ጐሣዎች በየቤተ ሰባቸው ሲቈጠሩ እነዚህ ናቸው።

21የሎቤናና የሰሜአ ጐሣዎች ከጌርሶን ወገን ናቸው፤ እነዚህ የጌርሶን ጐሣዎች ነበሩ። 22አንድ ወርና ከዚያ በላይ ሆኖአቸው የተቈጠሩት ወንዶች በሙሉ ብዛታቸው ሰባት ሺህ አምስት መቶ ነበር። 23የጌርሶን ጐሣዎች በምዕራብ በኩል ከማደሪያው ድንኳን ጀርባ ይሰፍራሉ። 24የጌርሶን ጐሣዎች ቤተ ሰቦች አለቃ የዳኤል ልጅ ኤሊሳፍ ይሆናል። 25የጌድሶናውያን ኀላፊነት በመገናኛው ድንኳን ማደሪያውንና ድንኳኑን፣ መደረቢያዎቹን እንዲሁም በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ ያለውን መጋረጃ፣ 26የአደባባዩን መጋረጃዎች፣ ማደሪያ ድንኳኑንና መሠዊያውን የሚጋርደውን የአደባባዩን መግቢያ መጋረጃ፣ ገመዶቹንና ከነዚሁ ጋር ተያይዞ አገልግሎት የሚሰጠውን ሁሉ መጠበቅ ይሆናል።

27የእንበረማውያን፣ የይስዓራውያን፣ የኬብሮናውያንና የዑዝኤላውያን ጐሣዎች ከቀዓት ወገን ናቸው፤ እነዚህ የቀዓት ጐሣዎች ነበሩ። 28አንድ ወርና ከዚያ በላይ ሆኖአቸው የተቈጠሩት ወንዶች በሙሉ ብዛታቸው ስምንት ሺህ ስድስት መቶ* ሲሆን፣ ቀዓታውያንም መቅደሱን የመጠበቅ ኀላፊነት ነበራቸው። 29የቀዓት ጐሣዎች ከማደሪያው ድንኳን በደቡብ በኩል ይሰፍራሉ። 30የቀዓት ጐሣዎች ቤተ ሰቦች አለቃ የዑዝኤል ልጅ ኤሊሳፈን ይሆናል። 31እነርሱም ታቦቱን፣ ጠረጴዛውን፣ መቅረዙን፣ መሠዊያዎቹን፣ ለመቅደሱ አገልግሎት የሚውሉትን ዕቃዎች፣ መጋረጃዎችንና ከነዚህ ጋር ተያይዞ አገልግሎት የሚሰጠውን ሁሉ ይጠብቃሉ። 32ዋናው የሌዋውያን አለቃ የካህኑ የአሮን ልጅ አልዓዛር ነው፤ እርሱም መቅደሱን ለመጠበቅ ኀላፊ በሆኑት ላይ ተሹሞ ነበር።

33የሞሖላውያንና የሙሳውያን ጐሣዎች ከሜራሪ ወገን ናቸው፤ እነዚህም የሜራሪ ጐሣዎች ነበሩ። 34አንድ ወርና ከዚያ በላይ ሆኖአቸው የተቈጠሩት ወንዶች ሁሉ ብዛታቸው ስድስት ሺህ ሁለት መቶ ነበር። 35የሜራሪም ጐሣዎች ቤተ ሰቦች አለቃ የአቢካኢል ልጅ ሱሪኤል ይሆናል፤ የሜራሪም ጐሣዎች ከማደሪያው ድንኳን በሰሜን በኩል ይሰፍራሉ። 36ሜራሪያውያንም የማደሪያውን ድንኳን ሳንቃዎች፣ መወርወሪያዎች፣ ምሰሶዎች፣ ምሰሶዎቹ የሚቆሙባቸውን እግሮች፣ የማደሪያ ዕቃዎችን ሁሉና ከነዚሁ ጋር ተያይዞ አገልግሎት የሚሰጠውን ሁሉ ለመጠበቅ ተሹመው ነበር። 37እንዲሁም የአደባባዩን ዙሪያ ምሰሶዎች ከነመቆሚያ እግሮቻቸው፣ ከነካስማቸውና ከነገመዶቻቸው ይጠብቃሉ።

38ሙሴ፣ አሮንና ልጆቹ ከማደሪያው ድንኳን በምሥራቅ በኩል በፀሐይ መውጫ ከመገናኛው ድንኳን ፊት ለፊት ይሰፍራሉ፤ እነርሱም እስራኤላውያንን ወክለው ማደሪያ ድንኳኑን ለመጠበቅ ኀላፊዎች ይሆናሉ፤ ወደ ማደሪያው ድንኳን የሚቀርብ ማንኛውም ሌላ ሰው ግን ይገደል።

*28 የዕብራይስጡ ትርጕም ከዚህ ጋር ይስማማል አንዳንድ የሰባ ሊቃናት ቅጆች ግን *ስምንት ሺህ ሦስት መቶ* ይላሉ።

3፥17 ዘፍ29፥34፤ 46፥11፤ዘፀ6፥16፤ ዘኍ1፥47፤ኢሱ21፥4፡ 6፤1ዜና15፥4፤23፥6፤ 2ዜና29፥12
3፥18 ዘፀ6፥17
3፥19 ዘፀ6፥18
3፥20 ዘፍ46፥11፤ ዘፀ6፥19
3፥21 ዘፍ46፥11፤ ዘፀ6፥17
3፥23 ዘኍ2፥18
3፥25 ዘፍ25፥9፤ ዘፀ26፥14፡36፤40፥2፤ ዘኍ4፥25፤7፥1
3፥26 ቍ31፤ዘፀ 27፥9፤35፥18፤ዘኍ 4፥26
3፥27 ዘፍ46፥11፤ ዘፀ6፥18፤ዘኍ4፥15፡ 37፤1ዜና26፥23
3፥28 ቍ15፤ዘኍ 4፥4፡15፤ዘፀ25፥8፤ 30፥13፤2ዜና30፥19፤ መዝ15፥1፤20፥2፤ ሕዝ44፥27
3፥29 ዘኍ1፥53
3፥30 ዘፀ6፥22
3፥31 ቍ26፤ዘፀ 25፥10-22፤23፡31፤ 26፥33፤ዘኍ1፥50፤ 4፥5፡15፤18፥3፤ዘዳ10፥ 1-8፤1ዜና28፥15፤2ዜና 5፥2፤ኢር3፥16፤52፥19
3፥32 ቍ28፤ዘፀ6፥ 23፤ዘኍ4፥19፤18፥3
3፥33 ዘፀ6፥19፤ ዘፍ46፥11
3፥34 ቍ15
3፥35 ዘኍ2፥25
3፥36 ዘኍ4፥32፤ 18፥3፤ዘፀ26፥15-25፡ 26-29፤35፥20-29፤ 36፥36
3፥37 ዘፀ27፥10-17፡19
3፥38 ዘኍ1፥53፤ 2፥3፤1ዜና9፥27፤23፥ 32፤ቍ7፡10፤ዘኍ1፥ 51፤18፥5

ይመሳሰላል። ሌዋውያን ተመልምለው የተሰበሰቡ ለጦርነት ሳይሆን በተቀደሰ የእግዚአብሔር ስፍራ የተለየ አገልግሎት እንዲሰጡ ነው።

3፥16 *በታዘዘው መሠረት*፤ ሙሴ ለእግዚአብሔር ትእዛዝ ግልጽና ሙሉ መታዘዝ ነበረው።

*3፥21-38*፤ በ1፥53 ላይ፣ "ድንኳናቸውን በምስክሩ ማደሪያ ዙሪያ" በማለት የተጠቀሰው ሐሳብ በዚህ ክፍል በሚገኙ አራት አንቀጾች ውስጥ በዝርዝር ተገልጾአል፦ (1) ጌድሶናውያን በምዕራብ በኩል (ቍ 21-26)፤ (2) ቀዓታውያን በደቡብ በኩል (ቍ 27-32)፤ (3) የሜራሪ ወገን በሰሜን በኩል (ቍ 33-37)፤ (4) ሙሴ፣ አሮንና ልጆቹ በምሥራቅ በኩል (ቍ 38)። የሌሎች ነገዶች አሰፋፈር በጣም ተወዳጅ ከሆነው ሰው ወገን ይጀምራል (1) ይሁዳ በምሥራቅ በኩል (2፥3)፤ (2) ሮቤል በደቡብ በኩል (2፥10)፤ (3) ኤፍሬም በምዕራብ በኩል (2፥18)፤ (4) ዳን በሰሜን በኩል (2፥25)። የሌዋውያን ነገድ በጣም ተወዳጅ ከሆነው ነገድ ፊት ይሆናል። የሌዋውያን ቤት መሪዎች ከሌሎቹ ነገድ መሪዎች ጋር ይመሳሰላሉ (የ1፥5-16 ማብ ይመ)። እንደ ሌሎቹ የነገድ መሪዎች ስም ሁሉ የሌዋውያን ነገድ መሪዎችም ስም የእግዚአብሔርን ስም በውስጣቸው ያዘሉ ናቸው።

3፥24 *ዳኤል*፤ "የእግዚአብሔር" ማለት ነው። *ኤሊሳፍ*፤ የዚህ ስም ትርጕም፣ "አምላኬ ጨምሮአል" ማለት ነው።

*3፥25-26*፤ የማደሪያው ድንኳን ሦስት መጋረጃዎች ወይም መከለያዎች ነበሩት፤ (1) በአደባባዩ መግቢያ ላይ (ቍ 26፤ 4፥26)፤ (2) በድንኳኑ መግቢያ በር ላይ (ቍ 25፡31፤ 4፥25)፤ (3) በቅድስተ ቅዱሳንና በቅድስት መካከል (4፥5)።

3፥27 *እንበረማውያን*፤ አሮን እንበረማዊ ነበር (ዘፀ 6፥20 ይመ)፤ ስለዚህ አሮንና ሙሴ ከቀዓት ቤተ ሰብ ነበሩ። ቀዓታውያን እጅግ ቅዱስ የሆኑ ንዋየ ቅዱሳትን እንዲጠብቁ ኀላፊነት ተሰጥቶአቸው ነበር (4፥4-18 ይመ)።

3፥28 *ስምንት ሺህ ስድስት መቶ*፤ በቍ 39 እንደ ተጠቀሰው ጠቅላላ የሌዋውያን ቍጥር ሃያ ሁለት ሺህ ነው፤ ይህም ከሰባት ሺህ አምስት መቶ ጌድሶናውያን (ቍ 22)፣ እዚህ ላይ ከተመለከቱ ስምንት ሺህ ስድስት መቶ ቀዓታውያንና ከስድስት ሺህ ሁለት መቶ የሜራሪ ወገኖች (ቍ 34) አጠቃላይ ድምር ላይ ሦስት መቶ ተቀንሶለት የሚቀረው ቍጥር ማለት ነው። ብዙዎች ጽሑፉን የገለበጠው ሰው እዚህ ላይ ተሳስቶ ይሆናል እንጂ ትክክለኛው ቍጥር ስምንት ሺህ ሦስት መቶ ነው ብለው ያምናሉ።

3፥30 *ኤሊሳፈን*፤ "አምላኬ ጠብቆአል" ማለት ነው። *ዑዝኤል*፤ "ብርታቴ እግዚአብሔር ነው" ማለት ነው።

3፥35 *ሱሪኤል*፤ "ዐለቴ እግዚአብሔር ነው" ማለት ነው። *አቢካኤል*፤ "አባቴ (መለኮታዊ) ኀይል ነው" ማለት ነው።

3፥38 *በፀሐይ መውጫ*፤ በጣም ክቡር ስፍራ ሲሆን፣ እስራኤላውያንን በመወከል ለሚሰጡት አገልግሎት ሙሴና አሮን በዚያ በኩል እንዲሆኑ ተደርጎ ነበር። *ሌላ ሰው ... ይገደል*፤ በማደሪያው ውስጥ የሚከናወነው አገልግሎት ሰዎች በእግዚአብሔር ፊት እንዲቀርቡ የሚረዳ የምሕረት አገልግሎት ነበር፤ ነገር ግን እንደ እግዚአብሔር ሐሳብ የሚፈጸም ስለ ሆነ ጥብቅ ሥነ ሥርዐት ያለው ነው። ወደ እርሱ ለመቅረብ በተወሰነ መንገድ ብቻ እንዲሆን ማድረጉ፣ እግዚአብሔር ከሁሉ በላይ ለመሆኑ ማስረጃ ነው (ቍ 10፤ 1፥51፤ 18፥7 ይመ)።

[39]አንድ ወርና ከዚያ በላይ ሆኖአቸው፣ ሙሴና አሮን በእግዚአብሔር ትእዛዝ በየጐሣቸው የቈጠሩአቸው የሌዋውያን ወንዶች ልጆች ጠቅላላ ብዛት ሃያ ሁለት ሺህ ነበር።

[40]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "በኵር ሆነው የተወለዱትን፣ አንድ ወርና ከዚያ በላይ የሆናቸውን እስራኤላውያን ወንዶች ሁሉ ቍጠር፤ ዝርዝራቸውንም ያዝ። [41]በኵር በሆኑት በእስራኤላውያን ልጆች ሁሉ ምትክ ሌዋውያንን እንዲሁም በኵር በሆኑት በእስራኤላውያን ከብቶች ሁሉ ምትክ የሌዋውያንን ከብቶች ለእኔ አድርጋቸው፤ እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነኝ።"

[42]ስለዚህ ሙሴ እግዚአብሔር ባዘዘው መሠረት የእስራኤላውያንን በኵር ሁሉ ቈጠረ፤ [43]አንድ ወርና ከዚያ በላይ ሆኖአቸው በየስማቸው የተመዘገቡት ወንድ በኵሮች ሁሉ ብዛታቸው ሃያ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ሰባ ሦስት ነበር።

[44]ደግሞም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [45]"በእስራኤላውያን በኵሮች ምትክ ሌዋውያኑን፣ በከብቶቻቸውም ምትክ የሌዋውያኑን ከብቶች ውሰድ፤ ሌዋውያኑም የእኔ ይሁኑ፤ እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነኝ። [46]ቍጥራቸው ከሌዋውያን ቍጥር በሁለት መቶ ሰባ ሦስት በልጦ የተገኘውን እስራኤላውያን በኵሮች ለመዋጀት፣ [47]ለእያንዳንዱ በኵር ክብደቱ ባለ ሃያ አቦሊ በሆነው በቤተ መቅደሱ ሰቅል″ ሚዛን ልክ አምስት አምስት ሰቅል ተቀበል፤ [48]የተረፉትንም እስራኤላውያን ለመዋጀት ገንዘቡን ለአሮንና ለልጆቹ ስጥ።"

[49]ስለዚህ ሙሴ በሌዋውያኑ ተዋጅተው ቍጥራቸው ትርፍ ከሆነው በኵሮች ላይ የመዋጃውን ገንዘብ ተቀበለ፤ [50]ከእስራኤላውያን በኵሮች ላይ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ልክ አንድ ሺህ ሦስት መቶ ስልሳ አምስት ሰቅል″ ሰበሰበ። [51]ሙሴም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ቃል በታዘዘው መሠረት የመዋጃውን ገንዘብ ለአሮንና ለልጆቹ ሰጣቸው።

**ቀዓታውያን**

# 4

እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [2]"ከሌዋውያን ወገን የቀዓት ዘር የሆኑትን በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ቍጠሩ። [3]እንዲሁም በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ይሠሩ ዘንድ ለማገልገል የሚመጡትን ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት የሆናቸውን ወንዶች ሁሉ ቍጠሩ።

[4]"በመገናኛው ድንኳን ውስጥ የቀዓታውያን ሥራ ንዋየ ቅዱሳቱን መጠበቅ ነው። [5]ሰፈሩ ሲነሳ አሮንና ልጆቹ ገብተው የሚከልለውን መጋረጃ ያውርዱ፤ የምስክሩንም ታቦት ይጠቅልሉበት፤ [6]ከዚያም በአቆስጣው ቍርበት ይሸፍኑት፤ ሙሉ በሙሉ ሰማያዊ የሆነ መጐናጸፊያ በላዩ ላይ ይዘርጉበት፤ መሎጊያዎቹንም በየቦታው ያስገቡ።

[7]"በገጸ ኅብስቱ ገበታ ላይ ሰማያዊ ጨርቅ ይዘርጉበት፤ በላዩም ላይ ወጭቶች፣ ጭልፋዎች፣ ጽዋዎች፣ ለመጠጥ ቍርባን የሚሆኑትን ማንቈርቈሪያዎች እንዲሁም ሁልጊዜ ከዚያ የማይታጣውን ኅብስት ያስቀምጡ። [8]በእነዚህም ላይ ቀይ ጨርቅ ይዘርጉ፤ የአቆስጣውን ቍርበት ደርበውም መሎጊያዎቹን በየቦታቸው ያስገቡ።

[9]"ደግሞም ሰማያዊ ጨርቅ ወስደው ማብሪያ መቅረዙንና መብራቶቹን፣ መኮስተሪያዎቹንና የኵስታሪ መቀበያዎቹን፣ እንዲሁም ለዚሁ አገልግሎት የሚውሉትን የዘይት ዕቃዎች ይሸፍኑበት። [10]ከዚያም ይህንና ከዚሁ ጋር የተያያዙትን ዕቃዎች ሁሉ በአቆስጣ ቍርበት መሸፈኛ ጠቅልለው በመሸከሚያ ሳንቃ ላይ ያስቀምጡት።

[11]"በወርቅ መሠዊያ ላይ ሰማያዊ ጨርቅ ዘርግተው በአቆስጣ ቍርበት በመሸፈን መሎጊያዎቹን በየቦታቸው ያስገቡ።

[12]"እንዲሁም በመቅደሱ ውስጥ ለአገልግሎት የሚሆኑትን ዕቃዎች በሙሉ ወስደው በሰማያዊ ጨርቅ በአቆስጣ ቍርበት በመሸፈን በመሸከሚያው ሳንቃ ላይ ያስቀምጡት።

[13]"ከናሱ መሠዊያ ላይ ዐመዱን ጠርገው ሐምራዊ ጨርቅ ያልብሱት፤ [14]ከዚያም ለመሠዊያው አገልግሎት የሚውሉትን ዕቃዎች በሙሉ፤ የእሳት ማንደጃዎቹን፣ ሜንጦዎቹን፣ የእሳት መጫሪያዎቹንና ጐድጓዳ ሳሕኖችን በላዩ ላይ ያድርጉ፤ በእነዚህም ላይ የአቆስጣ

″47 አምሳ አምስት ግራም ያህል ነው።
″50 አሥራ አምስት ኪ.ግ. ተኩል ያህል ነው።

3፥39 ቍ15፤ ዘኍ26፥62
3፥40 ቍ15፤ ዘኍ1፥2
3፥41 ቍ12፤ ዘሌ11፥44
3፥43 ቍ15፥39
3፥45 ቍ9፤ ዘሌ11፥44
3፥46 ዘፀ13፥13፤ ዘኍ18፥15
3፥47 ዘሌ27፥6:25፤ዘፀ30፥13
3፥48 ቍ50:51
3፥49 ቍ48
3፥50 ቍ41:45: 46-48
4፥2 ዘፀ30፥12
4፥3 ቍ23፤ዘኍ1፥47፤8፥25፤1ዜና23፥3: 24:27፤ዕዝ3፥8
4፥4 ቍ19፤ ዘኍ3፥28፤7፥9
4፥5 ዘኍ1፥51፤ ዘፀ26፥31:33፤ 1ዜና23፥26
4፥6 ዘፀ25፥5:13-15፤1ነገ8፥7፤2ዜና5፥8
4፥7 ዘፀ25፥30፤ 39፥36፤ዘሌ24፥6፤ ኤር52፥19
4፥8 ዘፀ26፥26-28
4፥9 ዘፀ25፥38
4፥10 ቍ12
4፥11 ዘፀ30፥1:4
4፥12 ቍ10፤ ዘኍ3፥31
4፥13 ዘፀ27፥1-8፤ ዘሌ1፥16፤ዘኍ3፥31
4፥14 ዘፀ31፥9፤ 27፥3:6፤ዘኍ7፥84፤ 1ዜና28፥17፤2ዜና4፥8 :11:16፤ኤር52፥18

3፥41 *እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤* እንዲደረግ የታዘዘው ሁሉ እውነተኛ አምላክ ከሆነ ከእግዚአብሔር ባሕርይ ጋር የሚሄድ ነው (የዘፀ 3፥14 ማብ ይመ)።

3፥43 *ሃያ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ሰባ ሦስት፤* ጠቅላላ ብዛቱ ከሁለት ሚሊዮን በላይ እንደ ሆነ ለሚገመት ሕዝብ ይህ ቍጥር እጅግ አነስተኛ ይመስላል፤ አጠቃላይ የሕዝቡን ቍጥር ቀንሶ ለማቅረብ መንገድ ለማግኘት ለሚደረገው ሙከራም እንደ አንድ የመከራከሪያ ነጥብ ሆኖ የሚቀርብ ነው (በዚህ ቍጥር መሠረት የተሰላው ጠቅላላ የሕዝብ ብዛት ሁለት መቶ አምሳ ሺህ ያህል ይሆናል)። አንዳንድ ሰዎች በዘፀአት ጊዜ የነበሩት በኵሮች ሁሉ በመጀመሪያው ፋሲካ ለእግዚአብሔር ተለይተው ስለ ነበር እነዚህ ሃያ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ሰባ ሦስት የበኵር ልጆች እስራኤላውያን ከግብፅ ከወጡ በኋላ እንደ ተወለዱ ይገምታል (ዘፀ 12፥22-23 ይመ)። ይሁን እንጂ የተጠቀሰው ሰው ወገን የተለየ የእግዚአብሔር አገልግሎት ስለ መመደቡ የሚጠቁም ክፍል ባለ መኖሩ ይህ ግምት ችግር ይፈጥራል።

4፥3 *ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት፤* በምዕራፍ ሦስት ላይ ዕድሜያቸው ከአንድ ወር በላይ የሆኑት ወንዶች ሁሉ ተዘርዝረዋል (3፥15)። በምዕራፍ አራት ላይ በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ለማገልገል ዕድሜያቸው የደረሰው ሌዋውያን ተገልጸዋል። ከሃያ ሁለት ሺህ ሌዋውያን ወንዶች ውስጥ (3፥39) ስምንት ሺህ አምስት መቶ ሰማንያዎቹ ለአገልግሎት የበቁ ነበሩ (ቍ 48)። ከ8፥24 አገልግሎት የሚጀመረው በሃያ አምስት ዓመት እንደ ነበር እንረዳለን፤ የመጀመሪያውም አምስት ዓመት በሌላው ሰው ሥር ሆኖ ልምምድ የሚያደርግበት ጊዜ ሊሆን ይችላል።

4፥4 *ንዋየ ቅዱሳቱ፤* ቀዓታውያን ንዋየ ቅዱሳቱን ለመጠበቅ ዋና ኀላፊነት የተሰጣቸው ቢሆንም ሞትን ስለሚያስከትል እንዲነኩአቸው (ቍ 15) ወይም እንዲመለከቱአቸው እንኳ (ቍ 20) አልተፈቀደላቸውም ነበር። አሮንና ልጆቹ ቀዓታውያን የሚሠሩትን ሥራ ሁሉ በጥብቅ ይቈጣጠሩ ነበር፤ ያልተሸፈኑ ወይም ያልተጋረዱ ንዋየ ቅዱሳትን መንካትና መመልከት የሚችሉት ካህናት ብቻ ነበሩ።

ቍርበት መሸፈኛ አልብሰው መሎጊያዎቹን በየቦታቸው ያስገቡ::

[15]"አሮንና ልጆቹ መቅደሱንና ዕቃዎቹን፣ ንዋየ ቅዱሳቱንም በሙሉ ሸፍነው ከጨረሱ በኋላ ሰፈሩ ለመንቀሳቀስ ዝግጁ ሲሆን ቀዓታውያን ለመሸከም ይምጡ፤ እንዳይሞቱ ግን ንዋየ ቅዱሳቱን መንካት የለባቸውም፤ ስለዚህ በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ያሉትን እነዚህን ዕቃዎች የሚሸከሙ ቀዓታውያን ናቸው::

[16]"የካህኑ የአሮን ልጅ አልዓዛር በመብራቱ ዘይት፣ ደስ የሚያሰኝ ሽታ ባለው ዕጣን፣ ዘወትር በሚቀርበው በእህል ቍርባንና በቅብዐ ዘይቱ ላይ ኀላፊነት ይኖረዋል፤ እንደዚሁም ማደሪያውንና በውስጡ ያለውን ሁሉ መቅደሱንና ዕቃዎቹን ጭምር ይጠብቃል::"

[17]*እግዚአብሔር* (ያሕዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [18]"የቀዓት ጐሣዎች ከሌዋውያን ተለይተው እንዳይጠፉ፤ [19]ወደ ንዋየ ቅዱሳቱ በሚቀርቡበትም ጊዜ በሕይወት እንዲኖሩ እንጂ እንዳይሞቱ አንተ ይህን አድርግላቸው፤ አሮንና ልጆቹ ወደ መቅደሱ ይግቡ፤ እያንዳንዱንም ሰው በየሥራው ላይ ይደልድሉት፤ ምን መሸከም እንዳለበትም ያስታውቁት:: [20]ቀዓታውያን ግን ንዋየ ቅዱሳቱን ለአንድ አፍታ እንኳን ለማየት አይግቡ፤ ቢገቡ ይሞታሉ::"

## ጌድሶናውያን

[21]*እግዚአብሔር* (ያሕዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [22]"ጌድሶናውያንንም በየቤተ ሰባቸውና በየጐሣቸው ቍጠራቸው፤ [23]ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት የሆናቸውን በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ይሠሩ ዘንድ ለማገልገል የሚመጡትን ወንዶች ሁሉ ቍጠር::

[24]"የጌድሶናውያን የሥራና የሸክም አገልግሎታቸው ይህ ነው፤ [25]እነርሱም የማደሪያውን መጋረጃዎች፣ የመገናኛውን ድንኳን፣ መደረቢያውንና በላዩ ላይ ያለውን የአቆስጣ ቍርበት፣ የመገናኛውን ድንኳን ደጃፍ መጋረጃዎች ይሸከሙ፤ [26]እንዲሁም በማደሪያውና በመሠዊያው ዙሪያ ያሉትን የአደባባዩን መጋረጃዎች፣ የአደባባዩን ደጃፍ መጋረጃ፣ ገመዶችና ለዚሁ አገልግሎት የሚውሉትን ዕቃዎች ሁሉ ይሸከሙ፤ በዚህም ያገልግሉ:: [27]የጌድሶናውያን አገልግሎት ሁሉ፣ ሸክምም ሆነ ሌላ ሥራ አሮንና ልጆቹ በሚሰጡት አመራር መሠረት ይሆናል:: የሚሸከሙትን ሁሉ በኀላፊነት ታስረክቧቸዋላችሁ:: [28]እንግዲህ የጌድሶናውያን ጐሣዎች በመገናኛው ድንኳን የሚኖራቸው አገልግሎት ይህ ነው፤ ተግባራቸውም በካህኑ በአሮን ልጅ በኢታምር አመራር ሥር ይሆናል::

## ሜራሪያውያን

[29]"ሜራሪያውያንን 'በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ቍጠራቸው፤ [30]እንደዚሁም በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ይሠሩ ዘንድ ለማገልገል የሚመጡትን ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት የሆናቸውን ወንዶች ሁሉ ቍጠር:: [31]በመገናኛው ድንኳን ውስጥ አገልግሎታቸውን በሚያከናውኑበት ጊዜ ተግባራቸው ይህ ነው፤ የማደሪያውን ሳንቃዎች፣ መወርወሪያዎች፣ ምሰሶዎችንና መቆሚያ እግሮቻቸውን፣ ይሸከማሉ፤ [32]እንደዚሁም በአደባባዩ ዙሪያ ያሉትን ምሰሶዎች ከነመቆሚያ እግሮቻቸው፣ ካስማዎችን፣ ገመዶችን፣ ከእነዚሁ ጋር ያሉትን ዕቃዎች ሁሉና ማንኛውም ለአገልግሎቱ አስፈላጊ የሆኑትን ነገሮች ሁሉ ይሸከማሉ:: እያንዳንዱ ሰው የሚሸከመውን ዕቃ ለይታችሁ በስሙ መድቡለት:: [33]እንግዲህ የሜራሪያውያን ጐሣዎች በካህኑ በአሮን ልጅ በኢታምር ሥር ሆነው በመገናኛው ድንኳን ሲሠሩ አገልግሎታቸው ይህ ነው::"

## የሌዋውያን ጐሣዎች ቈጠራ

[34]ሙሴ፣ አሮንና የማኅበረ ሰቡ አለቆች ቀዓታውያንን በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ቈጠሯቸው:: [35]ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት የሆኖአቸው በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ለማገልገል የመጡት ወንዶች ሁሉ፣ [36]በየጐሣቸው የተቈጠሩት ሁለት ሺህ ሰባት መቶ አምሳ ነበሩ:: [37]ይህ ከቀዓት ጐሣዎች ሁሉ በመገናኛው ድንኳን ያገለገሉት ሰዎች ጠቅላላ ድምር ነው:: ሙሴና አሮን፣ *እግዚአብሔር* (ያሕዌ) በሙሴ አማካይነት በሰጠው ትእዛዝ መሠረት እነዚህን ቈጠሯቸው::

[38]ጌድሶናውያን በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ተቈጥረው ነበር:: [39]በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ይሠሩ ዘንድ ለማገልገል የሚመጡት ከሠላሳ እስከ ሃምሳ ዓመት የሆናቸው ወንዶች ሁሉ፣ [40]በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው የተቈጠሩት ሁለት ሺህ ስድስት መቶ ሠላሣ ነበሩ:: [41]ይህ ከጌድሶን ጐሣዎች በመገናኛው ድንኳን ያገለገሉት ሰዎች ጠቅላላ ድምር ነው፤ *እግዚአብሔር* (ያሕዌ) በሰጠው ትእዛዝ መሠረት ሙሴና አሮን እነዚህን ቈጠሯቸው::

[42]ሜራሪያውያንም በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ተቈጥረው ነበር:: [43]በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ይሠሩ ዘንድ ለማገልገል የሚመጡት ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት የሆናቸው ወንዶች ሁሉ፣ [44]በየጐሣቸው የተቈጠሩት ሦስት ሺህ ሁለት መቶ ነበሩ:: [45]ይህ የሜራሪ ጐሣዎች ጠቅላላ ድምር ነው፤ *እግዚአብሔር* (ያሕዌ) በሙሴ አማካይነት በሰጠው ትእዛዝ መሠረት ሙሴና አሮን እነዚህን ቈጠሯቸው::

[46]ስለዚህ ሙሴ፣ አሮንና የእስራኤል አለቆች ሌዋውያኑን በየጐሣቸውና በየቤተ ሰባቸው ቈጠሯቸው፤ [47]ከሠላሳ እስከ አምሳ ዓመት የሆኖአቸው በመገናኛው ድንኳን ውስጥ አገል

4፥15 ቍ4፥5፤ዘፀ 28፥43፤ዘኍ1፥51፤3፥27፤7፥9፤2ሳሙ6፥6፡7
4፥16 ዘፀ25፥6፤ 29፥41፤ዘሌ6፥14-23፤ 10፥6፤29፥41፤ ዘኍ 3፥32
4፥19 ቍ15:27፤ ዘኍ3፥32
4፥20 ዘፀ19፥21
4፥23 ቍ3
4፥25 ዘፀ26፥14፤ 27፥10-18፤ዘኍ3፥25
4፥26 ዘፀ27፥9:16፤ ዘኍ3፥26
4፥27 ቍ19፤ ዘኍ3፥25:26
4፥28 ዘኍ7፥7፤ ዘፀ6፥23
4፥29 ዘፀ30፥12፤ ዘፍ46፥11
4፥31 ዘኍ3፥36
4፥32 ዘኍ3፥37
4፥33 ዘፀ38፥21
4፥34 ቍ2
4፥35 ቍ3
4፥37 ዘኍ3፥27
4፥38 ዘፍ46፥11
4፥43 ቍ3
4፥45 ቍ29
4፥46 ዘኍ1፥19
4፥47 ቍ3

4፥16 *የካህኑ ... አልዓዛር ... ኀላፊነት ይኖረዋል*፤ ሊቀ ካህናቱ ሕዝቡን በመወከል ወደ ንዋየ ቅዱሳቱ ሊቀርብ ይችላል:: እርሱ ይህን ማድረግ ባይችል ኖሮ ሕዝቡም ቀርቦ ማምለክ ባልቻለ ነበር::

ግሎት ለመስጠትና ለመሸከም የመጡት፣ [48]ቍጥራቸው ስምንት ሺህ አምስት መቶ ሰማንያ ነበሩ። [49]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሙሴ አማካይነት በሰጠው ትእዛዝ መሠረት እያ ንዳንዱ በየአገልግሎቱና በየሸክም ሥራው ተደለደለ፤ ስለዚህም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ቈጠራቸው።

## የሰፈሩ መንጻት

**5** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]"ተላላፊ የቆዳ በሽታ[ረ] ያለበትን ወይም ማንኛውም ዐይነት ፈሳሽ ከሰውነቱ የሚወ ጣውን ወይም ሬሳ በመንካቱ በሥርዐቱ መሠረት የረከሰውን ሰው ሁሉ ከሰፈር እን ዲያስወጡ እስራኤላውያንን እዘዝ፤ [3]ወን ድም ሆነ ሴት አስወጡ፤ እኔ በመካከላቸው የምኖርበትን ሰፈራቸውን እንዳያረክሱ ከሰ ፈር አስወጧቸው።" [4]እስራኤላውያን ይህ ንኑ አደረጉ፤ ሰዎቹንም ከሰፈር አስወጧቸው፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘውም መሠ ረት ፈጸሙ።

## የካሳ አከፋፈል

[5]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [6]"እስራኤላውያንን እንዲህ በላቸው፤ 'ወን ድም ሆነ ሴት በማናቸውም ረገድ ሌላውን ቢበድልና ከዚህም የተነሣ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘንድ ያለውን *ታማኝነት* ቢያጐድል ያ ሰው በደለኛ ነው [7]በሠራው ኀጢአት ይናዘዝ፤ ስለ በደሉም ሙሉ ካሳ ይክፈል፤ የተመደበበትም ካሳ ላይ አንድ አምስተኛ በመጨመር በደል ላደረሰበት ሰው ይስጥ፤ [8]ነገር ግን ይህ ሰው ካሳውን የሚቀበልለት ዘመድ ከሌለው ካሳው *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ስለሚሆን ማስተስረያ እንዲሆነው ከሚያ ቀርበው አውራ በግ ጋር ለካህኑ ይስጥ። [9]እስራኤላውያን የሚያመጧቸው የተቀደሱ ስጦታዎች ሁሉ ለተቀባዩ ካህን ይሆናሉ፤ [10]የእያንዳንዱ ሰው የተቀደሰ ስጦታ ለካህኑ ይሆናል፤ ለካህኑ የሚሰጠውም ሁሉ የራሱ ይሆናል።' "

## በአመንዝራነት ስለሚጠረጠሩ ሚስቶች

[11]ከዚህ በኋላ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [12]"እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ 'አንዲት ባለ ትዳር ሴት ወደ ሌላ ወንድ በማዘንበል ለባሏ ያላትን *ታማኝነት* አጕድላ፣ [13]ከሌላ ሰው ጋር ብት ተኛ፣ ይህም እጅ ከፍንጅ ባለመያዟ ምክ ንያት ይህ ከባሏ ቢደበቅ፣ የሚመሰክርባት ሰው ባይኖርና መርከሷም ባይገለጥ፣ [14]ባሏ የቅናት መንፈስ አድሮበት ቢጠረጥርና በር ግጥም ጐድፋ ብትገኝ ወይም ባሏ የቅናት መንፈስ አድሮበት ቢጠረጥርና እርሷ ግን ጐድፋ ባትገኝ፣ [15]ወደ ካህኑ ይውሰዳት፤ ስለ እርሷም አንድ ኪሎ[ሰ] ገብስ ዱቄት ለቍርባን ይውሰድ፤ በላዩ ላይ ዘይት አያፍ ስስበት፤ ዕጣንም አይጨምርበት፤ ይህ ስለ ቅናት የቀረበ የእህል ቍርባን በደልን የሚያሳስብ የመታሰቢያ ቍርባን ነውና።

4፥48 ዘኍ3፥39
4፥49 ዘኍ1፥47
5፥2 ዘሌ13፥2፡3፤ 15፥2፤21፥11፤ዘኍ 9፥6-10፤ማቴ9፥20
5፥3 ዘፀ29፥45፤ ዘሌ26፥12፤2ቆሮ6፥16
5፥6 ዘሌ5፥14-6፥7፤ 6፥2
5፥7 ዘሌ5፥5፡16፤ ሉቃ19፥8
5፥8 ዘሌ5፥15፤ 6፥6፡7
5፥9 ዘሌ6፥17
5፥10 ዘሌ7፥29-34
5፥12 ቍ19-21፤ ዘፀ20፥14
5፥13 ዘፀ20፥14
5፥14 ቍ30፤ምሳ 6፥34፤27፥4፤ መሓ8፥6
5፥15 ቍ18፡25፤ ዘፀ16፥36፤ዘሌ6፥20 ፤ሕዝ21፥23፤29፥16

[ረ]2 በተለምዶ ለምጽ ማለት ነው፤ የዕብራይስጡ ትርጕም ለምጽን ብቻ ሳይሆን የተለያዩ የቆዳ በሽታዎችን የሚያመለክት ነው።
[ሰ]15 የኢፍ መስፈሪያ አንድ አሥረኛ ማለት ነው።

5፥2 *ተላላፊ የቆዳ በሽታ፤* የዘሌ 13፥2 ማብ ይመ፤ ከሉቃ 5፥12-16፤ 17፥11-19 ጋር ያነጻጽሩ። *ማንኛውም ዐይነት ፈሳሽ፤* የዘሌ 15፥2 ማብ ይመ። አብዛኛውን ጊዜ እንደዚህ ዐይ ነት ፈሳሽ የሚመጣው ከአባለ ዘር አካባቢ ሲሆን፣ ረዘም ላለ ጊዜ ሊቆይ የሚችል ነው (ከሉቃ 8፥43-48 ጋር ያነጻጽሩ)። ወደ እግ ዚአብሔር ለመቅረብ ሕዝቡ ሁሉ፣ "ንጹሕ" መሆን እንደሚያስፈ ልጋቸው በዚህ ዐይነት ፈሳሽ የሚሠቃዩ ሰዎች ለኅብረተ ሰቡ ሁሉ ትምህርት የሚሆን ተጨባጭ ምሳሌዎች ነበሩ። *የረከሰው፤* ከአምልኮ ሥርዐት የተነሣ ከማኅበረ ሰቡ ጋር ሊሆን የማይገባው፣ ለማደሪያውና ንጹሕ ለሆነው የእግዚአብሔር አምልኮ መርከስ ምክንያት ሊሆን የሚችል ሰው ነው። ንጹሕ አለመሆን ሲባል በደፈናው ወይም በቃል ብቻ ተነግሮ የታለፈ አይደለም፤ እንደ ቈዳ በሽታና እንደ ፈሳሽ ያሉ በግልጽ በሚታዩ ተጨባጭ ነገ ሮች ላይ ያተኮረ ነበር። *ሬሳ፤* የመርከስ የመጨረሻው ተጨባጭ ምልክት ነው። የአስከሬኑ የመበስበስ ሂደትና የመፍረስ ሁኔታ ለሁሉ በግልጽ የሚታይ ነበር። ከሬሳ ጋር የአካል ንክኪ ማድረግ እርግጠኛ የመርከስ ምልክት ነበር፤ ተገቢ የሆነውን የመንጻት ሥርዐት እስኪፈጽሙ ድረስ በሕይወት ካሉት ሰዎች ጋር የሚደረገው ግንኙነት ለአጭር ጊዜ መቋረጥ አለበት። ከናዝራውያን የስእለት ሥርዐት ጋር ስላለው ግንኙነት የ6፥6 ማብ ይመ። ኢየሱስ ግን የሞተውንም በሕይወት ያለውንም ሰው ቀርቦ ይነካ ነበር፤ የኢያ ኢሮስንም ልጅ እጇን ይዞ ከሞት እንድትነሣ አድርጓአል (ሉቃ 8፥54)።

5፥3 *ወንድም ሆነ ሴት፤* ንጹሕ መሆንና አለመሆን ጾታን የሚለይ አይደለም። ዋናው ነገር እግዚአብሔር በሰፈሩ ውስጥ የመገኘቱ ጉዳይ ነበር፤ እርሱ ባለበት ስፍራ ርኩስ የሆነ ነገር ሊገኝ አይገባም። እግዚአብሔር በክርስቶስ አምነው ከዳኑ ሰዎች ጋር በሚኖርባት አዲሲቷ ኢየሩሳሌም (ራእ 21፥2-3)፣ ማንኛውም ዐይ ነት ርኩሰት ቦታ አይኖረውም (ራእ 21፥27)።

*5፥5-10፤* በዚህ ክፍል በሰዎች ዘንድ ስላለው ስለ እርስ በርስ በደል በተገለጸውና ቀደም ባለው አንቀጽ በተጠቀሰው በሥ ርዐት መሠረት መርከስ መካከል ያለው ግንኙነት በግልጽ ከሚታየው ውጫዊ ጕድለት ይበልጥ ውስጣዊና ድብቅ ወደ ሆነው የማኅ በረ ሰቡንም ንጽሕና የባሰ ወደሚበክለው ርእስ ጕዳይ መሄድ ሳይሆን አይቀርም። ንጹሕ ያለመሆናቸው ግልጽ ምልክት የሚ ታይባቸው ሰዎች ከበሽታው እስከሚነጹ ድረስ ከሰፈሩ ይገለላሉ። ነገር ግን በጣም አደገኛ የሆኑ በማኅበረ ሰቡ ውስጥ በሌሎች ላይ ግልጽ በደል ፈጽመው ምንም እንዳላደረጉ ለመመሳሰስ የሚሞ ክሩ ሰዎች ናቸው።

*5፥11-31፤* ቀደም ባሉት ሁለት አንቀጾች የተጠቀሰው ሐሳብ በዚህ ክፍል ካለው ጋር ያለው ግንኙነት በግልጽ ከሚታየው ኀጢ አት ጀምሮ ድብቅ ወደ ሆነው የግል ኀጢአት መሄዱ ነው። ስለ ንጽሕና የተጠቀሰው ሐሳብ በሰውነት ላይ ከሚታይ ምልክት ጀምሮ (ቍ 14) ከሌላው ጋር ባለው ግንኙነት የሚፈጠረውን ሁኔታ በመጥቀስ (ቍ 5-10)፣ ከዚያም ጥብቅ ወደ ሆነው ግን ኙነት፣ ይኸውም በጋብቻ የተጣመሩትን ባልና ሚስት ወደሚመ ለከት ንጽሕና ይገባል። በቈዳ ላይ የሚታየውን ጕድለት ለማረጋ ገጥ ከሚደረገው ሙከራ ይልቅ በትዳር ውስጥ ያለውን ታማኝ ነት ለማረጋገጥ የሚደረገው ሙከራ እጅግ አስቸጋሪ ነው፤ ስለዚህ ምዕራፉ ከሌሎቹ ክፍሎች ይልቅ በሰፊው ያተኮረው በዚህ ዋና ጕዳይ ላይ ነው።

5፥14 *የቅናት መንፈስ፤* ይህ መነሾው ትክክለኛ ነገር ተመሥርቶ ሊሆን ይችላል፤ መፍትሔም ሊገኝለት ያስፈልጋል። ዋናው ዐላማ ለተጐዳው ለባልየው የግል ስሜት በማሰብ ሳይሆን እግዚአብሔር በሕዝቡ መካከል እንደ መኖሩ መጠን ማኅበረ ሰቡ እንዲጠራ ነው (ቍ 3)። ሆኖም የምዕራፉ ዐላማ እምነት ሳይኖ ደል እንዲሁ ማስረጃ የሌላቸው ክሶች እንዳይቀርቡ ለማገድ ነው። በስሜቱ ተለዋዋጭ የሆነ ክፉ አሳቢ ባል፣ ታማኝ ሚስቱን ለመጨቅጨቅ ይህን ጽሑፍ መጠቀም አይችልም ነበር። *ጐድፋ ብትገኝ፤* ምዕራፉ የሚያተኵረው በአንድ ጕዳይ ላይ ነው፤ ይኸ ውም እግዚአብሔር የሚገኝበት ሰፈር (ቍ 3) ንጹሕ መሆን እን ዳለበት ነው።

*5፥15-28፤* በዚህ ክፍል የሚታየው ድርጊት ከባድና ጭካኔ የተሞላበት ይመስላል። በተለይ በዝሙት ጕዳይ በባሏ ክስ የቀረ በባት ሴት ለታማኝነቷ ወይም ለጥፋቷ ማስረጃ የሚሆን አሠራር ባይኖር ኖሮ ውጤቱ እጅግ የከፋ በሆነ ነበር። ሴትየዋ በመ

[16]“ ‘ካህኑ ሴትየዋን ያመጣትና *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት እንድትቆም ያደርጋታል፤ [17]ከዚያም የተቀደሰ ውሃ በሸክላ ዕቃ ቀድቶ በማደሪያው ድንኳን ካለው ወለል ጥቂት ዐፈር ቈንጥሮ በውሃው ውስጥ ይጨምራል። [18]ካህኑ ሴትየዋን *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት እንድትቆም ካደረገ በኋላ የጠጕሯን መሸፈኛ ይገልጣል፤ ስለ ቅናት የቀረበውን የመታሰቢያ ቍርባን በእጇ ያስይዛታል፤ ከዚያም ካህኑ ርግማን የሚያመጣውን መራራ ውሃ በእጁ ይይዛል። [19]ካህኑም ሴትየዋን ያስምላታል፤ እንዲህም ይላታል፤ “ሌላ ወንድ አብሮሽ ካልተኛ በትዳር ላይ ሆነሽ ወደ ርኩሰት ካላዘነበልሽ ይህ ርግማን የሚያመጣ መራራ ውሃ ጕዳት አያድርስብሽ፤ [20]ነገር ግን በትዳር ላይ እያለሽ ወደ ርኵሰት በማዘንበል ከባልሽ ሌላ ከወንድ ጋር በመተኛት ከጐደፍሽ”፣ [21]እዚህ ላይ ካህኑ እንዲህ በማለት ሴትየዋን በርግማን መሐላ ያስምላታል፤ “*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጭንሽን እያሰለለና[a] ሆድሽን እያሳበጠ በሕዝብሽ መካከል ርግማንና መሐላ ያድርግብሽ፤ [22]ይህን ርግማን የሚያመጣ ውሃ በጠጣሽ ጊዜም ሆድሽን ያሳብጠው፤ ጭንሽን ያስልለው፤” “ ‘ሴትየዋም፣ “አሜን፤ አሜን” ትበል።

[23]“ ‘ካህኑ እነዚህን መርገሞች በሰሌዳ ላይ ይጻፍ፤ በመራራውም ውሃ ይደምስሳቸው። [24]ርግማን የሚያመጣውንም ውሃ ሴትየዋ እንድትጠጣ ያድርግ፤ ውሃውም ወደ ሰውነቷ ገብቶ የመረረ ሥቃይ ያስከትልባታል። [25]ካህኑ ለቅናት የቀረበውን የእህል ቍርባን ይቀበላት፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ወዝውዞ ወደ መሠዊያው ያቅርበው። [26]ካህኑ የመታሰቢያ ቍርባን እንዲሆን እፍኝ የእህል ቍርባን ከዚያ ወስዶ በመሠዊያው ላይ ያቃጥለው፤ ከዚያም በኋላ ሴቲቱ ውሃውን እንድትጠጣ ያድርግ። [27]ራሷን በማጕደፍ ለባሏ ያላትን ታማኝነት አጕድላ ከሆነ፣ ርግማን የሚያመጣውን ውሃ እንድትጠጣ ሲደረግ ውሃው ወደ ሰውነቷ ገብቶ ክፉ ሥቃይ ያመጣባታል፤ ሆዷ ያብጣል[b]፤ ጭኗ ይሰልላል፤ በሕዝቧም ዘንድ የተረገመች ትሆናለች። [28]ዳሩ ግን ሴትየዋ ካልጐደፈችና ነውር ከሌለባት ከበደሉ ነጻ ትሆናለች፤ ልጆችም ትወልዳለች።

[29]“ ‘እንግዲህ የቅናት ሕግ ይህ ነው፤ አንዲት ሴት በትዳር ላይ እያለች ወደ ሌላ ሄዳ ከረከሰች፣ [30]ወይም አንድ ሰው ሚስቱን ከመጠርጠሩ የተነሣ የቅናት መንፈስ ሲያድርበት *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ያቁማት፤ ካህኑም ሕጉ በሙሉ በሴቲቱ ላይ ተፈጻሚነት እንዲኖረው ያድርግ። [31]ባልየውም ከበደል ንጹሕ ይሆናል፤ ሴትየዋ ግን በበደሏ ምክንያት የሚመጣውን ፍዳ ትቀበላለች።” ’

## የናዝራዊነት ሥርዐት

**6** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]“እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፣ ‘ወንድም ሆነ ሴት ናዝራዊ ይሆን ዘንድ ራሱን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ለመለየት ስእለት ቢሳል፣ [3]ከወይን ጠጅና ከሌላም ከሚያሰክር መጠጥ ይታቀብ፤ የወይንም ሆነ የሚያሰክር የሌላ መጠጥ ኾምጣጤ አይጠጣ፤ እንዲሁም የወይን ጭማቂ አይጠጣ፤ የወይን ፍሬም ሆነ ዘቢብ አይብላ። [4]በናዝራዊነቱ ወቅት ከወይን ተክል የሚገኘውን ማንኛውም ነገር፣ የወይኑን ዘር፣ ግልፋፊውንም እንኳ ቢሆን አይብላ።

[5]“ ‘ስእለት ተስሎ ራሱን በለየበት ጊዜ ሁሉ ምላጭ ራሱን አይንካው፤ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የተለየበት ጊዜ እስኪያበቃ ድረስ የተቀደሰ ይሁን፤ የራስ ጠጕሩንም ያሳድግ።

[a]21 *ሴቶች ያስወርዱ ወይም መካን ይሁኑ ማለት ነው።*
[b]27 *ትመክናለች ወይም ታስወርዳለች ማለት ነው።*

5፥18 ቍ15:19፤ ዘሌ10፥6፤1ቆሮ11፥6
5፥19 ቍ12:18:29
5፥20 ቍ12
5፥21 ኢሱ6፥26፤ 1ሳሙ14፥24፤ነህ 10፥29
5፥22 ቍ18፤መዝ 109፥18፤ዘዳ27፥15
5፥23 ኤር45፥1
5፥25 ዘሌ8፥27
5፥26 ዘሌ2፥2
5፥27 ኢሳ43፥28፤ 65፥15፤ኤር26፥6፤ 29፥18፤42፥18፤ 44፥12:22፤ዘካ8፥13
5፥29 ቍ19
5፥30 ቍ14
5፥31 ዘሌ5፥1
6፥2 ቍ5:6፤ዘፍ 28፥20፤ሐሥ21፥23፤ መሳ13፥5፤16፥17
6፥3 ዘሌ10፥9፤ 25፥5፤ሩት2፥14፤ መዝ69፥21፤ምሳ 0፥26፤ሉቃ1፥15
6፥5 መዝ52፥2፤ 57፥4፤59፥7፤ኢሳ 7፥20፤ሕዝ5፥1፤ 1ሳሙ1፥11

ጨረሻ ላይ ወደ ካህኑ መወሰዷ (ቍ 15) የምሕረትና የርኅራኄ ተግባር ነው። ታማኝነቷ ለሚያጠራጥር ሴት ይህን ያህል ጠንከር ያለ ሥርዐት መደረጉ ሕጉ በትዳር ላይ ታማኝነት ማጕደልን አጥብቆ እንደሚከለክል ያሳያል፤ ይህም ስለ ቀናተኛ ባል ብቻ የሚመለከት ጕዳይ አልነበረም። እንዲህ ዐይነቱን ታማኝነት ማጉደል ለጠቅላላው ኅብረተ ሰብ የሚተርፍ ችግር ነበረው፤ ስለዚህ ፍርዱ የሚሰጠው ከኅብረተ ሰቡ አንጻር ነበር።

5፥18 *የጠጕሯን መሸፈኛ ይገልጣል፤* ግልጽ መሆንን የሚያመለክት ሲሆን ጥፋተኛው ግን ፍርድና ሐዘን እንደሚጠብቀው ያሳያል። *ርግማን የሚያመጣውን መራራ ውሃ፤* ውሃው መራራ ጣዕም ነበረው ማለት ሳይሆን፣ መራራ ርግማን እንደሚያስከትል ለመግለጽ ነው። ይህ ውሃ ከጥንቆላ አሠራር ወይም ከሥነ ልቦና አንጻር ጫና የመፍጠር ዘዴ አለመሆኑን ለማሳየት የእግዚአብሔር ድርሻ በዚህ ውስጥ ምን እንደ ሆነ ተደጋግሞ ተገልጿል (ቍ 16:21:25)፤ ሴትየዋ በአካሏና በስሜቷ ለመራራው ውሃ የምታሳየው ሁኔታ በእርሷ ላይ የሚሰጠውን የውሳኔ ፍርድ ያፋጥነዋል፤ ነገር ግን ፍርዱ የሚሆነው ከእግዚአብሔር ነበር።

5፥21 *ጭንሽን እያሰለለና ሆድሽን እያሳበጠ፤* እዚህ ላይ የተሰጠው የአገላለጽ ዘይቤ (ደግሞ በቍ 22:27 ላይ)፣ ልጅ መውለድ አለመቻልንና ሴቲቱ ነፍሰ ጡር ከሆነችም ውርጃ እንደሚያስከትልባት የሚያመለክት ነው። ይህም ያለ አግባብ የተከሰሰች ሴት በሚገጥማት ዕድል ተለይቶ ይታወቃል (ቍ 28)። በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ አገሮች አንዲት ሴት ልጅ መውለድ ከተሳናት ይህ በሕይወቷ ውስጥ እጅግ ከፍተኛ ጕዳት ነበር። በጥንቱ ዓለም ሴት ከፍተኛ ክብርና ግምት የሚሰጣት ልጅ መውለድ ስትችል ስለ ነበር ይህን ዕድል መነፈግ አሳዛኝ ቅጣት ነበር።

6፥2 *ወንድም ሆነ ሴት፤* ወንዶችና ሴቶች በሚሳሉት ስእለት መካከል ያለውን ልዩነት ለመረዳት ም 30 ይመ። *ናዝራዊ ... ስእለት፤* ለተወሰነ ጊዜ ወይም ዕድሜ ልክም ቢሆን በተለየ መንገድ ራስን ለይቶ ለእግዚአብሔር በመስጠት በቅድስና መኖርን ያመለክታል። ብዙውን ጊዜ ትኵረት የሚሰጠው ናዝራዊ የሆነ ሰው ከምን ከምን እንደሚከለከል ነው፤ በእግዚአብሔር ፊት ግን በአምንታዊ መልኩ ራስን ለእርሱ መለየቱ ትልቅ ዋጋ አለው (ቍ 8 ይመ)። ይህ ራስን ለመግዛት የሚደረግ ስእለት ብቻ ሳይሆን ራስን ለእግዚአብሔር አሳልፎ ሙሉ በሙሉ የመስጠት ተግባርም ነው።

6፥4 *ማንኛውም ነገር፣ የወይኑን ዘር፤* የፈላ የወይን ጠጅ ወይም ጭማቂው ብቻ ሳይሆን፣ የወይኑ ፍሬና ግልፋፊው እንኳ የተከለከለ ነበር። አንድ ናዝራዊ ስእለት በሚሳልበት ጊዜ ራሱን ከሦስት ነገሮች አንጻር መቈጣጠር ነበረበት፤ (1) ምግቡን፣ (2)ገጽታውን፣ (3) ከሌሎች ሰዎች ጋር ያለውን ግንኙነት። እስራኤላዊ የሆነ ሁሉ እነዚህ ነገሮችን በተመለከተ ቍጥጥር ነበረበት፤ ናዝራዊ የሆነ ሰው ግን ቍጥጥሩ እጅግ ይጠብቅበት ነበር። ከዚህ ጋር ያለው ንጽጽር የክርስቶስን ሥቃይ በሚታሰብበት ወቅት ራስን ለክርስቶስ አሳልፎ በመስጠት በመንፈሳዊ ሕይወት ረገድ ክርስቲያኖች ጥሩ ምግብን በመተው የሚያደርጉት ጾም ሊሆን ይችላል።

6፥5 *ምላጭ ራሱን አይንካው፤* መሳ 13፥5 ይመ። ከተላጨው ውጭ ረጅም የናዝራዊ ጠጕር፣ ራሱን ለእግዚአብሔር ለይቶ በስእለት ለመስጠቱ በአካሉ ላይ የሚታየው ምልክት ነው፤ ከዘሌ 21፥5 ጋር ያነጻጽሩ።

[6]ራሱን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በለየበት ጊዜ ሁሉ ወደ ሬሳ አይቅረብ። [7]ራሱን ለእግዚአብሔር (ኤሎሂም) የለየበት ምልክት በራሱ ላይ ስላለ አባቱም ይሁን እናቱ፣ ወንድሙም ይሁን እኅቱ ቢሞቱ ለእነርሱ ሲል እንኳ ራሱን አያርክስ። [8]ራሱን በለየበት ጊዜ ሁሉ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የተቀደሰ ነው።

[9]" 'ድንገት ሰው አጠገቡ ሞቶ ለእግዚአብሔር የተለየበትን ጠጕሩን ቢያረክስበት፣ በሚነጻበት ዕለት ማለት በሰባተኛው ቀን ጠጕሩን ይላጭ። [10]በስምንተኛው ቀን ሁለት ዋኖስ ወይም ሁለት የርግብ ጫጩቶች ይዞ ወደ መገናኛው ድንኳን ደጃፍ ወደ ካህኑ ዘንድ ያምጣ። [11]ካህኑም አንዱን ለኀጢአት መሥዋዕት ሌላውን ማስተስረያ እንዲሆንለት የሚቃጠል መሥዋዕት አድርጎ ያቅርበው፤ በሬሳ አጠገብ በመገኘቱ ኀጢአት ሠርቶአልና። በዚያኑ ዕለት ጠጕሩን ይቀድስ። [12]ራሱን የተለየ ያደረገበትን ጊዜ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መቀደስ አለበት፤ እንዲሁም የአንድ ዓመት ተባት ጠቦት የበደል መሥዋዕት አድርጎ ያምጣ። ያለፉት ቀኖች አይቈጠሩም፤ በተለየበት ጊዜ ረክሶአልና።

[13]" 'እንግዲህ ናዝራዊ የመለየቱ ጊዜ ሲያበቃ ሥርዐቱ ይህ ነው፤ ወደ መገናኛው ድንኳን ደጃፍ እንዲመጣ ይደረጋል። [14]እዚያም መሥዋዕቱን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ያቅርብ፤ ይኸውም፣ እንከን የሌለበት የአንድ ዓመት ተባዕት ጠቦት ለሚቃጠል መሥዋዕት፣ እንከን የሌለበት የአንድ ዓመት እንስት ጠቦት ለኀጢአት መሥዋዕት እንዲሁም እንከን የሌለበት አውራ በግ ለኅብረት መሥዋዕት[ሀ] ሲሆን፣ [15]ከእነዚህም ጋር የሚቀርበውን የእህልና የመጠጥ ቍርባን ያለ እርሾ የተጋገረ ቂጣ ማለት ከላመ ዱቄት በዘይት የተለወሱ ዕንጎቻዎች እንዲሁም በስሱ የተጋገረና ዘይት የተቀባ ስስ ቂጣ ያምጣ።

[16]" 'ካህኑ እነዚህን የኀጢአት መሥዋዕትና የሚቃጠል መሥዋዕት በማድረግ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ያቀርባል። [17]በመሶብ ያለውን እርሾ የሌለበት ቂጣ እንዲሁም አውራ በጉን የኅብረት መሥዋዕት አድርጎ ከእህሉና ከመጠጡ ቍርባን ጋር ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ያቅርብ።

[18]" 'ከዚያም ናዝራዊው ተስሎ የተለየበትን ጠጕር በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ይላጨው፤ ጠጕሩንም ወስዶ ከኅብረቱ መሥዋዕት ሥር በሚነደው እሳት ውስጥ ይጨምረው።

[19]" 'ናዝራዊው ተስሎ የተለየበትን ጠጕር ከተላጨ በኋላ፣ ካህኑ የተቀቀለውን የአውራውን በግ ወርች እንዲሁም ከመሶቡ ላይ እርሾ የሌለበትን አንድ ወፍራምና አንድ ስስ ቂጣ ወስዶ ናዝራዊው ያስይዘው [20]ከዚያም ካህኑ የሚወዘወዝ መሥዋዕት በማድረግ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ይወዘውዛቸዋል፤ እነዚህም የተቀደሱ ናቸው። ከተወዘወዘው ፍርምባና ከቀረበው ወርች ጋር የተቀደሱ የካህኑ ድርሻ ይሆናሉ። ከዚህ በኋላ ናዝራዊው የወይን ጠጅ መጠጣት ይችላል።

[21]" 'ስእለቱን ለመፈጸም ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ለሚሳል ናዝራዊ ሕጉ ይኸው ነው፤ ሊቀርብ ከሚችለው በላይ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ለመስጠት ቃል ለሚገባው ነገር እንደ ናዝራዊነቱ በተሳለው መሠረት መሆን አለበት። በናዝራዊነት ሕግ መሠረት የተሳለውን ስእለት መፈጸም ይገባዋል።' "

## የካህናት ቃለ ቡራኬ

[22]እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን አለው፤ [23]"አሮንንና ልጆቹን እንዲህ በላቸው፤ 'እስራኤላውያንን በምትባርኩበት ጊዜ እንዲህ በሉአቸው፤

[24]" 'እግዚአብሔር (ያህዌ) ይባርክህ፤
ይጠብቅህም፤
[25]እግዚአብሔር (ያህዌ) ፊቱን ያብራልህ፤
ይራራልህም፤
[26]እግዚአብሔር (ያህዌ) ፊቱን ይመልስልህ፤
ሰላሙንም ይስጥህ።' "

[27]" በዚህ ሁኔታ ስሜን በእስራኤላውያን ላይ ያደርጋሉ፤ እኔም እባርካቸዋለሁ።"

## ማደሪያው ድንኳን ሲመረቅ የቀረቡ ስጦታዎች

**7** ሙሴ የማደሪያ ድንኳኑን ተክሎ ካበቃ በኋላ ማደሪያ ድንኳኑንና ዕቃዎቹን ሁሉ

6፥6 ዘሌ21፥1-3፤ ዘኍ19፥11-22
6፥7 ዘኍ9፥6
6፥9 ቍ18፤ ዘሌ14፥9
6፥10 ዘሌ5፥7፤ 14፥10:11
6፥11 ዘፍ8፥20፤ ዘፀ29፥36፤30፥10
6፥12 ዘሌ5፥15፤ 12፥6
6፥13 ሐሥ21፥26፤ ዘሌ14፥11
6፥14 ዘፀ12፥5፤ ቍ11፤ዘሌ3፥1፤4፥3፤ 5፥15፤14፥10
6፥15 ዘሌ2፥1፤ 6፥14፤ዘፍ35፥14፤ ዘፀ29፥2
6፥16 ዘሌ1፥3፤ ቍ10:11
6፥17 ዘፀ29፥41፤ ዘሌ3፥1፤23፥13
6፥18 ቍ9፤ ሐሥ21፥24
6፥19 ዘሌ7፥12
6፥20 ዘሌ7፥30: 34፤27፥9፤መክ9፥7
6፥21 ቍ2:13
6፥23 ዘዳ21፥5፤ 1ዜና23፥13
6፥24 ዘፍ28፥3፤ ዘዳ28፥3-6፤1ሳሙ 2፥9፤መዝ17፥8፤ 28፥9፤128፥5
6፥25 ዘፍ43፥29፤ ኢዮ29፥24፤መዝ4፥6 ፤25፥16፤31፥16፤80፥ 3፤86፥16፤119፥29: 135
6፥26 መዝ4፥6:8፤ 44፥3፤29፥11፤37፥11: 37፤127፥2፤ኢሳ 14፥7፤ኤር33፥6፤ ዮሐ14፥27
6፥27 ዘዳ28፥10፤ 2ሳሙ7፥23፤2ዜና 7፥14፤ነህ9፥10፤ኤር 25፥29፤ሕዝ36፥23
7፥1 ቍ84:88፤ ዘፀ30፥26፤40፥9:10: 17፤2ዜና7፥9

[ሀ]14 በተለምዶ የድነት መሥዋዕት ማለት ነው

6፥6 *ሬሳ፤* የ5፥2 ማብ ይመ። ናዝራዊ የሆነ ሰው የሞተው ሰው ከራሱ ቤተ ሰብ እንኳ ቢሆን፣ ሬሳ እንዳይነካ ይከለከላል (ቍ 7፤ ዘሌ 21፥1-3 ከዚህ ጋር ያገናዝቡ)።

*6፥9-12፤* ናዝራዊ የሆነ ሰው ስእለት ሲሳል በሚገባ ተረድቶ መወሰን በሚቻለው ጕዳይ ላይ መሆን ነበረበት። ይህ ክፍል ሳይታሰብና ከዕቅድ ውጭ በዕለት ኑሮ የሚያጋጥሙትን ነገሮች የሚመለከት ነው።

*6፥13-20፤* ናዝራዊው የስእለቱ ወቅት በተፈጸመ ጊዜ የሚያቀርበው መሥዋዕት ብዛት ያለውና ውድ ከመሆኑም በላይ ራሱን በለየባቸው ወራት ሕይወቱ ሙሉ በሙሉ ለጌታ የተገዛ እንደ ነበር የሚገልጽ ነበር።

6፥21 *ለ ... ናዝራዊ ሕጉ ይኸው ነው፤* እንደዚህ ዐይነቱ የማጠቃለያ ዐረፍተ ነገር በክፍሉ የተጠቀሰውን ፍሬ ነገር ለመደምደም ብቻ ሳይሆን የይዘቱንም ሐሳብ ለማጽናት ነው።

*6፥24-26፤* የአሮን የቡራኬ ቃል ነው። የእግዚአብሔር ስም ሦስት ጊዜ ተደጋግሞ መጠቀሱ አጽንዖት ለመስጠትና በቍ 27፣ "ስሜን በእስራኤላውያን ላይ ያደርጋሉ" የሚለው አገላለጽ ክብደት እንዲኖረው ነው። በእያንዳንዱ ቍጥር ላይ ሁለት የቡራኬ ቃላት ይገኛሉ፤ የስንኞቹ ርዝመት በተወሰነ መጠን እየጨመረ የሚሄድ ነው (በዕብራይስጡ የመጀመሪያው ቍጥር ሦስት ቃላት፣ ሁለተኛው ቍጥር አምስት፣ ሦስተኛው ደግሞ ሰባት ቃላት አሏቸው)።

6፥25 *ፊቱን ያብራልህ፤* ተቀባይነትና ሞገስ ማግኘትን ያመለክታል።

6፥26 *ሰላሙንም፤* ቃሉ ፍጹም መረጋጋትን የሚያሳይ ሲሆን፣ አንዳች መዛባት በሌለበት ሁኔታ በፍጹም ደኅንነት መገኘትን የሚያመለክት እንጂ፣ የጦርነትን አለመኖር ብቻ የሚያሳይ አይደለም። እንዲህ ዐይነቱ ሰላም የሚገኘው ከእግዚአብሔር ብቻ ነው።

*7፥1-89፤* ስለ ማደሪያው ድንኳን አተካከል የሚገልጸውን ደግሞም ደመናው ወርዶ እንዴት ድንኳኑን እንደ ሸፈነና የእግዚአብሔር ክብር እንዴት ስፍራውን እንደ ሞላው በመዘገብ የሚደመደመውን ዘፀ 40 ይመ። ከአምስቱ የሙሴ መጻሕፍት ውስጥ (ብሔረ ኦሪት) በጣም ረጅም የሆነው ይህ ምዕራፍ ተደ

ቀባቸው፤ ቀደሳቸውም፤ እንደዚሁም መሠዊያውንና ዕቃዎቹን በሙሉ ቀባቸው፤ ቀደሳቸውም። 2ከዚያም የእስራኤል አለቆች ሆነው ከተቈጠሩት ነገዶች ኀላፊዎች የነበሩት የየቤተ ሰቡ መሪዎች ስጦታቸውን አቀረቡ። 3ስድስት የተሸፈኑ ሠረገሎችና ዐሥራ ሁለት በሬዎች ይኸውም ከያንዳንዱ አለቃ አንዳንድ በሬ እንዲሁም ከየሁለቱ አለቆች አንድ ሠረገላ ስጦታ አድርገው ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት አመጡ፤ እነዚህንም በማደሪያው ድንኳን ፊት አቀረቧቸው።

4እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ 5"በመገናኛው ድንኳን ለአገልግሎት እንዲውሉ እነዚህን ከእነርሱ ተቀበል፤ ለእያንዳንዳቸውም ለአገልግሎታቸው በሚያስፈልጋቸው መጠን ለሌዋውያኑ ስጣቸው።"

6ስለዚህ ሙሴ ሠረገሎቹንና በሬዎቹን ወስዶ ለሌዋውያኑ ሰጣቸው፤ ለጌድሶናውያን ለአገልግሎታቸው በሚያስፈልጋቸው መጠን ሁለት ሠረገሎችና አራት በሬዎች ሰጠ። 8ለሜራሪያውያንም ለአገልግሎታቸው በሚያስፈልጋቸው መጠን አራት ሠረገሎችና ስምንት በሬዎች ሰጠ። እንግዲህ እነዚህ ሁሉ በካህኑ በአሮን ልጅ በኢታምር ኀላፊነት የሚመሩ ነበሩ። 9በኀላፊነት የተሰጧቸውን ንዋያተ ቅዱሳት በትከሻቸው መሸከም ስለነበረባቸው፣ ሙሴ ለቀዓታውያን ምንም አልሰጣቸውም።

10መሠዊያው በተቀባበት ቀን አለቆች የመሠዊያውን መቀደስ ምክንያት በማድረግ ስጦታዎችን አመጡ፤ በመሠዊያውም ፊት አቀረቡ። 11እግዚአብሔርም (ያህዌ) ሙሴን፣ "የመሠዊያውን መቀደስ ምክንያት በማድረግ እያንዳንዱ አለቃ ስጦታውን በቀን በቀኑ ያቅርብ" አለው።

12በመጀመሪያው ቀን ስጦታውን ያቀረበው ከይሁዳ ነገድ የአሚናዳብ ልጅ ነአሶን ነበር፤

13ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ 14ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ 15ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ 16ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ 17እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የአሚናዳብ ልጅ ነአሶን ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

18በሁለተኛው ቀን የይሳኮር አለቃ የሶገር ልጅ ናትናኤል ስጦታውን አመጣ፤

19ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ 20ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ 21ለሚቃጠል መሥዋዕት፣ አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ 22ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ 23እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የሶገር ልጅ ናትናኤል ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

24በሦስተኛው ቀን የዛብሎን ሕዝብ አለቃ የኬሎን ልጅ ኤልያብ ስጦታውን አመጣ፤

25ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ 26ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ 27ለሚቃጠል መሥዋዕት፣ አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ 28ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ 29እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የኬሎን ልጅ ኤልያብ ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

30በአራተኛው ቀን የሮቤል ሕዝብ አለቃ

7፥2 ዘኍ1፥5-16፡19
7፥3 ዘፍ45፥19፤ 1ሳሙ6፥7-14፤ 1ዜና13፥7
7፥7 ዘኍ4፥24-26፡28
7፥8 ዘኍ4፥31-33
7፥9 ዘኍ4፥4፡15
7፥10 ቍ1፤ዘፀ 29፥36፤2ዜና7፥9
7፥12 ዘኍ1፥7
7፥13 ቍ85፤ዘፀ 27፥3፤30፥13፤ዘሌ2፥1፤27፥3-7፤ዘኍ 6፥15፤15፥4
7፥14 ቍ20፡86፤ ዘፀ25፥6፤1ነገ7፥50፤ 2ነገ25፥14፤2ዜና 4፥22፤24፥14
7፥15 ዘፀ24፥5፤ 29፥3፤ዘኍ28፥11፤ ዘሌ1፥3
7፥16 ዘሌ4፥3
7፥17 ዘሌ3፥1፤ ዘኍ1፥7
7፥18 ዘኍ1፥8
7፥20 ቍ14
7፥24 ዘኍ1፥9
7፥30 ዘኍ1፥5

ጋጋሚ በሆነ አገላለጽ በመጠቀም የዐሥራ ሁለቱ ነገድ አለቆች፣ ለማደሪያው ድንኳን አገልግሎት ይውል ዘንድ ለእግዚአብሔር ያቀረቡትን የከበረና ተመሳሳይ የሆነ ስጦታን ይዘረዝራል። ለእግዚአብሔር የቀረበው መሥዋዕት ከአሮን ቡራኬ (6፥24-26) ቀጥሎ መጻፉ ትክክለኛ አቀማመጥ ይመስላል፤ እግዚአብሔር ሕዝቡን ለመባረክ ለገባው ቃል ምላሽ በመስጠት የነገድ አለቆቹ ለዐሥራ ሁለት ተከታታይ ቀናት የበዓል መልክ ባለው ሁኔታ ለእግዚአብሔር ስጦታ አቀረቡ።

*7፥12-78፤* የዐሥራ ሁለቱ ነገድ አለቆች ስም ቀደም ብሉ በ1፥5-15፤ 2፥3-32 ተገልጾአል። ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ያቀረቡት ቅደም ተከተልም ከጕዞ አሰላለፋቸው ጋር ተመሳሳይ ነበር፤ ይኸውም፣ መጀመሪያ ከማደሪያው ድንኳን በስተ ምሥራቅ የሰፈሩት ሦስት ነገዶች (ይሁዳ፣ ይሳኮርና ዛብሎን፤ 2፥3-9፤ 7፥12፡18፡24)፣ ሁለተኛ በስተ ደቡብ በኩል የሰፈሩት ሦስት ነገዶች (ሮቤል፣ ስምዖንና ጋድ፤ 2፥10-16፤ 7፥30፡36፡42)፣ ሦስተኛ በስተ ምዕራብ በኩል የሰፈሩት ሦስት ነገዶች (ኤፍሬም፣ ምናሴና ብንያም፤ 2፥18-24፤ 7፥48፡54፡60)፣ በመጨረሻም በስተ ሰሜን በኩል የሰፈሩት ሦስት ነገዶች (ዳን፣ አሴርና ንፍታሌም፤ 2፥25-31፤ 7፥66፡72፡78)።

የሰዲዮር ልጅ ኤሊሱር ስጦታውን አመጣ፤ [31]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቊር ባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [32]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወ ርቅ ጭልፋ፣ [33]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [34]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [35]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆና ቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የሰዲዮር ልጅ ኤሊ ሱር ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[36]በአምስተኛው ቀን የስምዖን ሕዝብ አለቃ የሱሪሰዳይ ልጅ ሰለሚኤል ስጦታውን አመጣ፤

[37]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቊር ባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [38]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ [39]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይ ፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [40]ለኀጢአት መሥ ዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [41]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚ ቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የሱሪሰዳይ ልጅ ሰለሚኤል ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[42]በስድስተኛው ቀን የጋድ ሕዝብ አለቃ የራ ጉኤል ልጅ ኤሊሳፍ ስጦታውን አመጣ፤ [43]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቊር ባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሰላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [44]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወ ርቅ ጭልፋ፣ [45]ለሚቃጠል መሥዋዕት፣ አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [46]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [47]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆና ቸው አምስት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የራጉኤል ልጅ ኤሊሳፍ ያቀ ረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[48]በሰባተኛው ቀን የኤፍሬም ሕዝብ አለቃ የዓሚሁድ ልጅ ኤሊሳማ ስጦታውን አመጣ፤ [49]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቊር ባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [50]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወ ርቅ ጭልፋ፣ [51]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [52]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [53]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አም ስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አም ስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እን ግዲህ የዓሚሁድ ልጅ ኤሊሳማ ያቀረ በው ስጦታ ይህ ነበር።

[54]በስምንተኛው ቀን የምናሴ ሕዝብ አለቃ የፍደሱር ልጅ ገማልኤል ስጦታውን አመጣ፤ [55]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቊር ባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [56]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወ ርቅ ጭልፋ፣ [57]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [58]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [59]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆና ቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የፍደሱር ልጅ ገማል ኤል ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[60]በዘጠነኛው ቀን የብንያም ሕዝብ አለቃ የጋዴዮን ልጅ አቢዳን ስጦታውን አመጣ፤ [61]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቊር ባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [62]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወ ርቅ ጭልፋ፣ [63]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [64]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [65]እንዲሁም ለኅብረት

7፥36 ዘኍ1፥6
7፥42 ዘኍ1፥14
7፥48 ዘኍ1፥10
7፥53 ዘኍ1፥10
7፥54 ዘኍ1፥10
7፥60 ዘኍ1፥11

መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የጋዴዮን ልጅ አቢዳን ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[66]በአሥረኛው ቀን የዳን ሕዝብ አለቃ የአሚሳዳይ ልጅ አኪዔዘር ስጦታውን አመጣ፤ [67]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [68]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ [69]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው የበግ ጠቦት፣ [70]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [71]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የአሚሳዳይ ልጅ አኪዔዘር ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[72]በዐሥራ አንደኛው ቀን የአሴር ሕዝብ አለቃ የኤክራን ልጅ ፋግኤል ስጦታ አመጣ፤ [73]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [74]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ [75]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው ተባዕት የበግ ጠቦት፣ [76]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [77]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት ፍየል እንዲሁም አንድ ዓመት የሆናቸው አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የኤክራን ልጅ ፋግኤል ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[78]በዐሥራ ሁለተኛው ቀን የንፍታሌም ሕዝብ አለቃ የዔናን ልጅ አኪሬ ስጦታውን አመጣ፤ [79]ስጦታውም፣ እያንዳንዱ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የተሞላ በቤተ መቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ ሠላሳ ሰቅል የሚመዝን የብር ሳሕንና ሰባ ሰቅል የሚመዝን ከብር የተሠራ ጐድጓዳ ሳሕን፣ [80]ዐሥር ሰቅል የሚመዝን በዕጣን የተሞላ የወርቅ ጭልፋ፣ [81]ለሚቃጠል መሥዋዕት አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግ፣ አንድ ዓመት የሆነው ተባዕት የበግ ጠቦት፣ [82]ለኀጢአት መሥዋዕት አንድ ተባዕት የፍየል ጠቦት፣ [83]እንዲሁም ለኅብረት መሥዋዕት የሚቀርብ ሁለት በሬ፣ አምስት አውራ በግ፣ አምስት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበሩ። እንግዲህ የዔናን ልጅ አኪሬ ያቀረበው ስጦታ ይህ ነበር።

[84]መሠዊያው በተቀባ ቀን የእስራኤል አለቆች የመሠዊያውን መቀደስ ምክንያት በማድረግ ያቀረቡአቸው ስጦታዎች እነዚህ ናቸው፤ ዐሥራ ሁለት የብር ሳሕኖች፣ ዐሥራ ሁለት ከብር የተሠሩ ጐድጓዳ ሳሕኖችና ዐሥራ ሁለት የወርቅ ጭልፋዎች፣ [85]እያንዳንዱ የብር ሳሕን መቶ ሠላሳ ሰቅል፣ እያንዳንዱም ጐድጓዳ ሳሕን ሰባ ሰቅል፣ ባጠቃላይም የብር ሳሕኖቹ ክብደት በመቅደሱ ሰቅል ሚዛን ሁለት ሺህ አራት መቶ ሰቅል ይመዝን† ነበር። [86]ዕጣን የሞላባቸው ዐሥራ ሁለቱ የወርቅ ጭልፋዎችም እያንዳንዳቸው በመቅደሱ ሰቅል ሚዛን ዐሥር ሰቅል መዘኑ፤ ባጠቃላይ የወርቅ ጭልፋዎቹ ክብደት አንድ መቶ ሃያ ሰቅል‡ ነበር። [87]ለሚቃጠል መሥዋዕት የቀረቡት እንስሳት የእህል ቍርባናቸውን ጨምሮ ድምራቸው፦ ዐሥራ ሁለት ወይፈን፣ ዐሥራ ሁለት አውራ በግ፣ ዐሥራ ሁለት አንድ ዓመት የሆናቸው ተባዕት የበግ ጠቦቶች ሆነ፤ እንዲሁም ለኀጢአት መሥዋዕት የቀረቡ ዐሥራ ሁለት ተባዕት ፍየሎች ነበሩ። [88]ለኅብረት መሥዋዕት የቀረቡት እንስሳት ድምር ሃያ አራት በሬ፣ ሥልሳ አውራ በግ፣ ሥልሳ ተባዕት ፍየልና ሥልሳ አንድ ዓመት የሆናቸው ተባዕት የበግ ጠቦቶች ነበር፤ እንግዲህ መሠዊያው ከተቀባ በኋላ ለመሠዊያው መቀደስ የቀረቡ ስጦታዎች እነዚህ ናቸው።

[89]ሙሴ ከእግዚአብሔር (ያህዌ) ጋር ለመነጋገር ወደ መገናኛው ድንኳን በገባ ጊዜ ከምስክሩ ታቦት መክደኛ በላይ በሁለቱ ኪሩቤል መካከል ድምፅ ሲናገረው ሰማ፤ አነጋገረውም።

## የመብራቶቹ አቀማመጥ

**8** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]"አሮንን ተናገረው፤ እንዲህም በለው፤ 'ሰባቱን መብራቶች በየቦታቸው በምታስቀምጥበት ጊዜ በመቅረዙ ፊት ለፊት ላለው አካባቢ ብርሃን ይሰጣሉ።' "

†85 ሃያ ስምንት ኪ.ግ. ያህል ነው።
‡86 አንድ ኪ.ግ. ተኩል ያህል ነው።

7፥66 ዘኍ1፥12
7፥72 ዘኍ1፥13
7፥78 ዘኍ1፥15
7፥84 ቍ1፡10፡ 14፤ዘኍ4፥14
7፥85 ቍ13
7፥86 ቍ13
7፥87 ቍ13፡15፡16
7፥88 ቍ1፡10፡ 17፤ዘፍ32፥14
7፥89 ዘፀ40፥2፤ 16፥34፤29፥42፤40፥2 ዘኍ3፥31፤መዝ80፥1፤ 99፥1
8፥2 ዘፀ25፥37

*7፥84-88*፤ በዐሥራ ሁለት ቦታ የተመደቡ ስጦታዎችን ጠቅላላ ብዛት ያመለክታል።

7፥89፤ በእግዚአብሔርና በነቢዩ መካከል ግንኙነት መመሥረቱን ያሳያል፤ ግንኙነቱም ግቡን በሚገባ መትቶአል፤ ሕዝቡም ከእግዚአብሔር ጋር የሚያነጋግረው መካከለኛ የሚሆን ሰው አግኝቶአል።

8፥2 *በመቅረዙ ፊት ለፊት ላለው አካባቢ፤* በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ቅድስት በተባለው ስፍራ ማለት ነው (ዘፀ 25፥37፤ 26፥33፤ 27፥21 ይመ)።

[3]አሮንም እንዲሁ አደረገ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት መብራቶቹ በመቅረዙ ላይ ሆነው ፊት ለፊት እንዲያበሩ አስቀመጣቸው:: [4]የመቅረዙ አሠራር እንዲህ ነበር፤ ከመቆሚያው እስከ አበቦቹ ያለው ከተቀጠቀጠ ወርቅ የተሠራ ሲሆን፣ የመቅረዙም አሠራር እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ ባሳየው መሠረት ነበር::

## የሌዋውያን ለአገልግሎት መለየት

[5]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [6]“ሌዋውያኑን ከእስራኤላውያን መካከል ለይተህ በሥርዐቱ መሠረት አንጻቸው:: [7]ስታነጻቸውም እንዲህ አድርግ፤ በሚያነጻ ውሃ እርጫቸው፤ ገላቸውን በሙሉ ተላጭተው ልብሳቸውን ይጠቡ፤ በዚህም ይንጹ:: [8]በዘይት ከተለወሰ ልም ዱቄት የእህል ቍርባን ጋር አንድ ወይፈን ይውሰዱ፤ ከዚያም ለኀጢአት መሥዋዕት የሚሆን ሌላ ወይፈን አንተ ትወስዳለህ:: [9]ሌዋውያኑን ወደ መገናኛው ድንኳን ፊት አምጣ፤ መላውንም የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ሰብስብ፤ [10]ሌዋውያኑን በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት አቅርብ፤ ከዚያም እስራኤላውያን እጃቸውን ይጫኑባቸው:: [11]ከዚያም አሮን ሌዋውያኑን የእግዚአብሔርን (ያህዌ) አገልግሎት ለማከናወን ዝግጁ እንዲሆኑ ከእስራኤላውያን መካከል እንደሚወዘወዝ መሥዋዕት በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ያቅርባቸው::

[12]“ሌዋውያኑ እጃቸውን በወይፈኖቹ ራስ ላይ ከጫኑ በኋላ ለሌዋውያኑ ማስተስረያ ይሆን ዘንድ የኀጢአት መሥዋዕት፣ ሌላውን የሚቃጠል መሥዋዕት አድርገህ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) አቅርባቸው:: [13]ከዚያም ሌዋውያኑን በአሮንና በልጆቹ ፊት አቁማቸው፤ እንደሚወዘወዝ መሥዋዕት አድርገህም ለእግዚአብሔር (ያህዌ) አቅርባቸው:: [14]በዚህ መሠረት ሌዋውያኑን ከእስራኤላውያን ትለያቸዋለህ፤ እነርሱም የእኔ ይሆናሉ::

[15]“ሌዋውያኑን ካነጻሐቸውና እንደሚወዘወዝ መሥዋዕት አድርገህ ካቀረብሀቸው በኋላ አገልግሎታቸውን ለመፈጸም ወደ መገናኛው ድንኳን ይማጣሉ፤ [16]እነርሱም ሙሉ በሙሉ የእኔ እንዲሆኑ የተሰጡኝ እስራኤላውያን ናቸው፤ ከማንኛቸውም እስራኤላዊት በተወለደ በኵር ወንድ ልጅ ምትክ የራሴ እንዲሆኑ ወስጃቸዋለሁ:: [17]ከሰውም ሆነ ከእንስሳ በእስራኤል የተወለደ ማንኛውም በኵር ተባዕት የእኔ ነው፤ በግብፅ የነበረውን በኵር ሁሉ በመታሁ ጊዜ የእኔ እንዲሆኑ ለይቻቸዋለሁ:: [18]በእስራኤል በተወለዱት ተባዕት በኵሮች ሁሉ ምትክም ሌዋውያኑን ወስጃለሁ:: [19]እስራኤላውያንን ወክለው በመገናኛው ድንኳን ውስጥ የሚፈጸመውን አገልግሎት እንዲያከናውኑና እስራኤላውያን ወደ ተቀደሰው ስፍራ ቢቀርቡ እንዳይቀሠፉ ያስተሰርዩላቸው ዘንድ፣ ከእስራኤላውያን ሁሉ መካከል ሌዋውያኑን ስጦታ አድርጌ ለአሮንና ለልጆቹ ሰጥቻቸዋለሁ::”

[20]ሙሴና አሮን እንዲሁም የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ሁሉ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት በሌዋውያኑ አደረጉ:: [21]ሌዋውያኑ ራሳቸውን አነጹ፤ ልብሶቻቸውንም አጠቡ፤ ከዚያም አሮን እንደሚወዘወዝ መሥዋዕት በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት አቀረባቸው፤ እንዲነጹም ማስተስረያ አደረገላቸው:: [22]ከዚህ በኋላ ሌዋውያኑ በአሮንና በልጆቹ ኀላፊነት ሥር ሆነው ድንኳን ውስጥ የሚፈጸመውን አገልግሎት ለማከናወን ገቡ:: እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት አስፈላጊውን በሌዋውያኑ አደረጉ::

[23]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [24]“ሌዋውያንን የሚመለከተው ደንብ ይህ ነው፤ በመገናኛው ድንኳን አገልግሎት ለመሳተፍ ሃያ አምስት ዓመትና ከዚያ በላይ የሆናቸው ወንዶች ይመጣሉ፤ [25]ዕድሜያቸው አምሳ ዓመት ሲሞላ ግን መደበኛ አገልግሎታቸውን ይተዉ፤ ዳግም ሥራ አይሥሩ:: [26]ከዚያ በኋላ ወንድሞቻቸው በመገናኛው ድንኳን ሥራቸውን በሚያከናውኑበት ጊዜ

8፥4 ዘፀ25፥9:18:36
8፥6 ዘሌ22፥2፤ ኢሳ1፥16፤52፥11
8፥7 ዘፍ35፥2፤ዘኍ 6፥9፤19፥9:17፤31፥23 ፤ዘሌ14፥8:9፤ ዘዳ21፥12
8፥8 ዘሌ2፥1፤ 4፥3፤ዘኍ15፥8-10
8፥9 ዘፀ40፥12፤ ዘሌ8፥3
8፥10 ዘሌ3፥2፤ ሐሥ6፥6
8፥11 ዘፀ29፥24
8፥12 ዘፀ29፥10: 36፤ዘሌ1፥3፤4፥3፤ ዘኍ6፥11
8፥13 ዘፀ29፥24
8፥14 ዘኍ3፥12
8፥15 ዘፀ29፥24፤ 40፥2
8፥16 ዘኍ1፥20፤ 3፥12
8፥17 ዘፀ4፥23፤ 13፥2፤22፥29
8፥18 ዘኍ3፥12
8፥19 ዘኍ3፥7: 9፤16፥46
8፥21 ቍ7:12፤ ዘፍ35፥2፤ዘኍ16፥47
8፥22 ቍ11
8፥24 ዘፀ38፥21፤ 1ዜና23፥3
8፥25 ዘኍ4፥3
8፥26 ቍ11

*8፥5-26፤* የሌዋውያንን መንጻት የሚገልጽ ሲሆን፣ አሮንና ልጆቹ ለክህነት መቀባታቸውን ከሚናገረው ታሪክ ጋር (ዘሌ 8) ሲነጻጸር ይችላል:: ሌዋውያን የካህናት ረዳቶች እንደ መሆናቸው መጠን መቀደሳቸውን የሚገልጸውም አነጋገር ስለ ካህናት ከተነገረው ይለያል:: ለካህናት፣ “ቅዱሳን” ሆኑ ሲል፣ ለሌዋውያን “ንጹ” ይላል፤ ለካህናት፣ “ተቀቡ፣ ታጠቡ” ሲል፣ ለሌዋውያን ያላቸውን ልብስ አጠቡ፤ ካህናት ደም እንዲነካቸው ሲደረግ፣ ሌዋውያን ግን በላያቸው ላይ ይወዘወዝ ነበር::

8፥7 *ገላቸውን በሙሉ ተላጭተው፤* ከለምጽ የነጻው ሰው እንደሚያደርገው (ዘሌ14፥8)፣ ሙሉ በሙሉ መንጻታቸውን የሚያመለክት ድርጊት ነው::

*8፥10 እስራኤላውያን እጃቸውን ይጫኑባቸው፤* ሌዋውያን ሕዝቡን ወክለው በእግዚአብሔር ፊት የሚቆሙ ነበሩ፤ በእነርሱ ላይ እጃቸውን ሲጭኑ፣ ሕዝቡ ይህን ውክልና መቀበላቸውን ያረጋግጣል (ቍ 16-18 ይመ)::

8፥16 *የእኔ፤* የ3፥9 ማብ ይመ::

*8፥19 ሌዋውያኑን ስጦታ አድርጌ ለአሮንና ለልጆቹ ሰጥቻቸዋለሁ፤* ሌዋውያን ለተለየ አገልግሎት ለእግዚአብሔር ብቻ የተሰጡ ነበሩ (ቍ 14 ይመ):: በመገናኛው ድንኳን የአምልኮ አገልሎት ካህናትን ይረዱአቸው ዘንድ እግዚአብሔር የእርሱ የሆኑትን ሌዋውያን ለካህናቱ ሰጣቸው:: *እስራኤላውያን ... እንዳይቀሠፉ፤* የእስራኤል ሕዝብ ወደ ተቀደሰው ማደሪያ ድንኳን ቅጥር ግቢ በመዝለቅ እንዳይተላለፉ፣ ሌዋውያን በሕዝቡና በድንኳኑ መካከል በመስፈር መከለያ ሆነው ነበር (የ1፥53 ማብ ይመ)::

*8፥20 እግዚአብሔር ሙሴን ባዘዘው መሠረት፤* ቍ 4: 22፤ 1፥54፤ 2፥3፤ 3፥16:51፤ 4፥49፤ 5፥4፤ 9፥5:23 ይመ:: እግዚአብሔር የአምልኮንና የአመጋገብን ሥርዐት በሚመለከት የሰጠውን ትእዛዝ ሙሴና እስራኤላውያን በፍጹም ታዘዋል፤ ይሁን እንጂ ከም 11 ጀምሮ ሕዝቡ ፍቅር በተሞላው በእግዚአብሔር ባሕርይ ላይ ማጕረምረማቸውና ታማኝነት እያጎደሉ መሄዳቸው ከነበራቸው ታዛዥነት ጋር ሲነጻጸር የሚገርም ነው::

8፥24 *ሃያ አምስት ዓመት፤* የ4፥3 ማብ ይመ፤ በንጉሣዊ አገዛዝ ሥር የአሠራራቸው ሁኔታ እጅግ በመለወጡ (1ዜና 23፥26 ይመ)፤ ዳዊት ሌዋውያን አገልግሎት የሚጀምሩበትን ዕድሜ ወደ ሃያ ዓመት ዝቅ አድርጎት ነበር (1ዜና 23፥24:27 ይመ):: ይሁን እንጂ በ4፥3 እና በዚህ ጥቅስ መካከል የሁኔታዎች ለውጥ ይኖራል ብሎ መገመት ያስቸግራል:: በመሆኑም እነዚህ ሁለት ክፍሎች የአምስት ዓመት የአገልግሎት ልምምድ ጊዜን እንደ ሚያመለክቱ የአይሁድ መምህራን የሚሰጡት ግምት ተቀባይነት ያለው ይመስላል::

ያግዟቸዋል እንጂ ራሳቸው መሥራት የለባቸውም:: ኀላፊነታቸውን እንዲወጡ የምታስማራቸው በዚህ መልኩ ነው::"

## የፋሲካ በዓል

**9** ከግብፅ ምድር በወጡ በሁለተኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ወር እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን በሲና ምድረ በዳ ተናገረው፤ እንዲህም አለው፤ [2]"እስራኤላውያን በተወሰነው ጊዜ የፋሲካን በዓል እንዲያከብሩ አድርግ፤ [3]በዓሉንም በዚህ ወር በዐሥራ አራተኛው ቀን ፀሐይ በምትጠልቅበት ጊዜ በተወሰነው ሕግና ሥርዐት መሠረት ሁሉ አክብሩ::"

[4]ስለዚህ ሙሴ ፋሲካን እንዲያከብሩ ለእስራኤላውያን ነገራቸው፤ [5]እነርሱም በመጀመሪያው ወር፣ በዐሥራ አራተኛውም ቀን ፀሐይ በምትጠልቅበት ጊዜ በሲና ምድረ በዳ ፋሲካ አደረጉ፤ እስራኤላውያን እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ሁሉንም አደረጉ::

[6]አንዳንዶቹ ግን የሰው ሬሳ በመንካታቸው በሥርዐቱ መሠረት ረክሰው ስለ ነበር በዚያን ዕለት የፋሲካን በዓል ማክበር አልቻሉም፤ ስለዚህም በዚያኑ ዕለት ወደ ሙሴና ወደ አሮን መጥተው፣ [7]ሙሴን፣ "በሬሳ ምክንያት ረክሰናል፤ ታዲያ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) መሥዋዕት ከሌሎቹ እስራኤላውያን ጋር ሆነን በተወሰነው ጊዜ እንዳናቀርብ ለምን እንከለከላለን?" አሉት::

[8]ሙሴም፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ስለ እናንተ የሚያዘውን እስካውቅ ድረስ ጠብቁ" ሲል መለሰላቸው::

[9]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [10]"እስራኤላውያንን እንዲህ በላቸው፤ 'ከእናንተ ወይም ከዘሮቻችሁ ማንኛውም ሰው በሬሳ ምክንያት ቢረክስ ወይም ሩቅ መንገድ ቢሄድ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ፋሲካ ማክበር ይችላል፤ [11]ይህንም በሁለተኛው ወር፣ በዐሥራ አራተኛው ቀን ፀሐይ በምትጠልቅበት ጊዜ ያክብሩ፤ የፋሲካውንም በግ እርሾ ከሌለበት ቂጣና ከመራራ ቅጠል ጋር ይብሉት:: [12]እስከ ነጋ ድረስ ከዚህ ምንም አያስተርፉ፤ ከዐጥንቱም ምንም አይስበሩ፤ ፋሲካን በሚያከብሩበት ጊዜ ሥርዐቱን በሙሉ መጠበቅ አለባቸው:: [13]በሥርዐቱም መሠረት ንጹሕ የሆነ ወይም ሩቅ መንገድ ያልሄደ ሰው ፋሲካን ሳያከብር ቢቀር፣ ያ ሰው የእግዚአብሔርን (ያህዌ) መሥዋዕት በተወሰነው ጊዜ ኣላቀረበምና ከወገኖቹ ፈጽሞ ይለይ፤ ያም ሰው የኀጢአቱን ዋጋ ይቀበላል::

[14]" 'በመካከላችሁ የሚኖር መጻተኛ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ፋሲካ ለማክበር ቢፈልግ በሕጉና በሥርዐቱ መሠረት መፈጸም አለበት፤ ለመጻተኛውም ሆነ ለአገሬው ተወላጅ የሚኖራችሁ ሕግ አንድ ይሁን' "

## ከማደሪያው በላይ የነበረው ደመና

[15]ማደሪያው በተተከለ ዕለት ደመናው የምስክሩን ድንኳን ሸፈነው፤ ከምሽት እስከ ንጋት ድረስ ማደሪያውን የሸፈነው ደመና እሳት ይመስል ነበር:: [16]ይህ በዚህ ሁኔታ ቀጠለ፤ ደመናው ማደሪያውን ሸፈነው፤ በሌሊትም የእሳት መልክ ነበረው:: [17]ደመናው ከድንኳኑ ላይ በሚነሣበት ጊዜ እስራኤላውያን ጕዞአቸውን ይጀምሩ ነበር፤ ደመናው በሚቆምበት ቦታ ደግሞ ይሰፍሩ ነበር፤ [18]እስራኤላውያን ጕዞ የሚጀምሩትም ሆነ የሚሰፍሩት በእግዚአብሔር (ያህዌ) ትእዛዝ ነበር:: ደመናው በድንኳኑ ላይ በሚቈይበት ጊዜ ሁሉ ከሰፈር አይንቀሳቀሱም ነበር:: [19]ደመናው በድንኳኑ ላይ ብዙ ቀን ቢቈይም እስራኤላውያን የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ትእዛዝ

9፥1 ዘፀ40፥2፤ ዘኍ1፥1
9፥2 ቍ7፤ዘፀ12፥11
9፥3 ዘፀ12፥6:42፤ 12፥2-11:43-49፤ ዘሌ23፥5-8፤ ዘዳ 16፥1-8
9፥4 ቍ2፤ዘፀ12፥11
9፥5 ቍ1:3፤ ዘፀ12፥6
9፥6 ዘፀ18፥15፤ ዘሌ5፥3፤13፥3፤21፥11 ፤ዘኍ27፥2
9፥7 ቍ2
9፥8 ዘፀ18፥15፤ ዘሌ24፥12፤ዘኍ15፥34፤27፥5:21፤መዝ 85፥8
9፥10 ቍ6፤ 2ዜና30፥2
9፥11 ዘፀ12፥6:8
9፥12 ቍ3፤ዘፀ12፥8:46፤ዮሐ19፥36
9፥13 ዘፍ17፥14
9፥14 ዘፀ12፥19:43
9፥15 ዘፀ13፥21፤ 26፥30፤33፥16፤ 38፥21
9፥16 ዘፀ40፥38
9፥17 ቍ21፤ 1ቆሮ10፥1
9፥18 ዘፀ40፥37
9፥19 ዘፀ40፥37፤ ዘሌ8፥35

8፥26 *ያግዙአቸዋል፤* አንድ ሌዋዊ አገልግሎቱን የሚፈጽምበት አምሳ ዓመት ዕድሜው ከደረሰ በኋላ (ቍ 25 ይመ) አነስተኛ ዕድሜ ያላቸውን የሥራ ባልደረቦቹን መርዳት (በበዓላት ጊዜ ሊሆን ይችላል) አይከለከልም፤ ሆኖም ቀደም ብሎ ይሠራ የነበረውን ዐይነት ከባድ ተግባር እንዲያከናውን አይደረግም::

*9፥1-14፤* ይህ ክፍል በአራት የተከፈለ ነው:- (1) ፋሲካን ያከብሩ ዘንድ የተሰጠው ትእዛዝ (ቍ 1-5)፤ (2) በአምልኮ ሥርዐት መሠረት ንጹሕ ስላልሆኑ ሰዎች የተነሣ ጥያቄ፤ (3) እግዚአብሔር በቂ ምክንያት ያላቸው ዘግይተው ፋሲካ እንዲያደርጉ መፍቀዱ፤ ያለ በቂ ምክንያት ችላ ብለው ጊዜውን የሚያሳልፉ ግን እንዲቀጡ ማድረጉ (ቍ 9-13)፤ (4) በፋሲካ ጊዜ የመጻተኛው መብት (ቍ 14):: የመጀመሪያው ፋሲካ የተደረገው በግብፅ ነበር (ዘፀ 12 ይመ)፤ ሁለተኛውም ከአንድ ዓመት በኋላ እዚህ በሲና ተከበረ:: በእስራኤል አለመታዘዝና እግዚአብሔር በእርሷ ላይ በወሰነው ፍርድ ምክንያት (ም 14)፣ እስራኤል ወደ ተስፋዪቱ ምድር እስከምትገባ ድረስ ፋሲካን ኣላከበረችም (ኢያ 5፥10 ይመ)::

9፥1 *በሁለተኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ወር፤* በዚህ ምዕራፍ የተጠቀሱ ድርጊቶች የተፈጸሙት በም 1 ላይ ያለው የሕዝብ ቈጠራ ከመደረጉ በፊት ነው (1፥1 ይመ)::

9፥3 *ፀሐይ በምትጠልቅበት ጊዜ፤* በአይሁድ ልማድ ይህ ጊዜ አንድ ቀን የሚያበቃበትና ቀጣዩ ቀን የሚጀምርበት እንደ ሆነ ይቈጠራል::

9፥7 *የእግዚአብሔርን፣ መሥዋዕት... እንዳናቀርብ ለምን እንከለከላለን?* በአምልኮው ሥርዓት መሠረት ንጹሕ ያልሆኑ ሰዎች እግዚአብሔርን "በመንፈስና በእውነት" ለማምለክ (ዮሐ 4፥24) ከፍተኛ ፍላጎት ነበራቸው::

9፥10 *ማክበር ይችላል፤* እነዚህ ሰዎች ፋሲካን ከማክበር ፍጹም እንዳይገለሉ ከአንድ ወር በኋላ የሚያከብሩበት አማራጭ ቀን ከእግዚአብሔር ቸርነት የተነሣ ተሰጥቶአቸዋል (ቍ 11):: ንጹሕ ሆኖ አለመገኘት በአማኙና በጉባኤው መካከል ልዩነት መፍጠሩና በኅብረት እንዳይሳተፍ ማገዱ እውነት መሆኑን ጌታ ይገልጻል፤ በቸርነቱ ግን አማራጩን ያዘጋጃል::

9፥12 *ከዐጥንቱም ምንም አይስበሩ፤* ኢየሱስ ("የፋሲካን በግ" 1ቆሮ 5፥7፤ ከዮሐ 1፥29 ጋር ያነጻጽሩ) በተሰቀለ ጊዜ በቅዱሳት መጻሕፍት የተጻፈው ይፈጸም ዘንድ (ዮሐ 19፥36) ከእርሱ ዐጥንት አንድም አልተሰበረም:: በተጨማሪም ዘፀ 12፥46፤ መዝ 34፥20 ይመ::

9፥13 *ፋሲካን ሳያከብር ቢቀር... ፈጽሞ ይለይ፤* አዲስ ኪዳንም ተገቢ ባልሆነ አቀራረብና ጥንቃቄ በጐደለው ሁኔታ ቀርቦ ከጌታ እራት መካፈል ፍርድ እንደሚያስከትል በብርቱ ያሳስባል (1ቆሮ 11፥28-30):: የዘፀ 12፥15 ማብ ይመ::

9፥14 *መጻተኛ፤* በፋሲካ ክብረ በዓል ከመሳተፉ በፊት መገረዝ ያስፈልገው ነበር (ዘፀ 12፥48)::

9፥15 *ደመናው ... ሸፈነው፤* የዘፀ 13፥21፤ 40፥34 ማብ ይመ:: የእግዚአብሔር ክብር በማደሪያው ድንኳን ላይ ስፍር እንደ ነበር ደመናው በግልጽ ያመለክት ነበር:: ይህ ደመና ተራ አለመሆኑ የሚታወቀው የመገናኛው ድንኳን ተከላ ሲያልቅ ወዲያው በመታየቱ ብቻ ሳይሆን ማታ ማታም የእሳት መልክ የነበረው በመሆኑ ነው:: እግዚአብሔርም የሕዝቡን ጕዞ በደመናው አማካይነት ይመራ ነበር (ቍ 17-18)::

9፥18 *በእግዚአብሔር ትእዛዝ፤* ደመናው የሚወርደውም የሚወጣውም በእግዚአብሔር ትእዛዝ ነበር::

ይጠብቃሉ እንጂ ተነሥተው አይጓዙም:: [20]አንዳንድ ጊዜ ደመናው በድንኳኑ ላይ የሚቈየው ለጥቂት ቀን ብቻ ነበር፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ትእዛዝ ይሰፍራሉ፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ትእዛዝ ጕዞ ይጀምራሉ፤ [21]አንዳንድ ጊዜ ደግሞ ደመናው ከምሽት እስከ ንጋት ብቻ ይቈያል፤ ደመናው ንጋት ላይ ሲነሣም ጕዞአቸውን ይጀምራሉ፤ ቀንም ይሁን ሌሊት ደመናው ከተነሣ ጕዞ ይጀምራሉ:: [22]ደመናው በድንኳኑ ላይ ለሁለት ቀንም ይሁን ለወር ወይም ለዓመት ቢቈይ፣ እስራኤላውያን በሰፈር ይቈያሉ እንጂ ጕዞአቸውን አይቀጥሉም:: [23]*በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ትእዛዝ ይሰፍራሉ፤ *በእግዚአብሔርም* (ያህዌ) ትእዛዝ ይጓዛሉ፤ እነርሱም በሙሴ አማካይነት የተሰጠውን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ይጠብቁ ነበር::

## የብር መለከቶች

**10** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]“ከተቀጠቀጠ ብር ሁለት መለከት አብጅ፤ ማኅበረ ሰቡን ለመጥሪያና ከሰፈራቸው እንዲነሡም ለመቀስቀሻ አድርጋቸው:: [3]ሁለቱ መለከቶች ሲነፉ ማኅበረ ሰቡ በሙሉ በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ አንተ ዘንድ ይሰብሰብ፤ [4]ነገር ግን አንዱ መለከት ብቻ ከተነፋ አለቆች ማለት የእስራኤል ጐሣ መሪዎች አንተ ዘንድ ይሰብሰቡ፤ [5]መለከቱ ከፍ ባለ ድምፅ ሲነፋ በስተ ምሥራቅ የሰፈሩት ነገዶች ጕዞ ይጀምሩ፤ [6]መለከቱ ከፍ ባለ ድምፅ ለሁለተኛ ጊዜ ሲነፋ በስተ ደቡብ የሰፈሩት ነገዶች ጕዞ ይጀምሩ፤ ከፍ ያለው ድምፅ ጕዞ ለመጀመር ምልክት ይሆናል:: [7]ማኅበሩን ለመሰብሰብ መለከቶች ይነፉ፤ ነገር ግን ድምፁ አይጩኽ::

10፥2 ቍ8:9፤ዘኍ 31፥6፤33፥3፤ነህ4፥18፤12፥35፤መዝ47፥5፤98፥6፤150፥3፤ኢር4፥5፡19፤6፥1፤ሆሴ5፥8፤8፥1፤አሞ3፥6፤ኢል2፥1፡15
10፥4 ዘፀ18፥21
10፥5 ቍ14
10፥6 ቍ18
10፥7 ኢር4፥5፤6፥1፤ሕዝ33፥3፤ኢል2፥1፤1ቆሮ14፥8
10፥8 ዘፍ9፥12፤ዘኍ15፥14፤35፥29
10፥9 ዘፍ8፥1፤ዘፀ3፥9፤ዘሌ23፥24፤መሳ2፥18፤6፥9፤1ሳሙ10፥18፤2ነገ13፥4፤2ዜና13፥12፤መዝ106፥4:42
10፥10 ዘሌ1፥3፤3፥1፤11፥44፤23፥24፤ዘኍ6፥14፤28፥11፤1ሳሙ20፥5:24፤2ነገ4፥23፤2ዜና8፥13፤መዝ81፥3፤ኢሳ1፥13፤ሕዝ45፥17፤46፥6፤አሞ8፥5
10፥11 ዘፀ38፥21፤40፥17፤ዘኍ9፥17
10፥12 ዘፍ14፥6፤ዘጸ1፥1፤33፥2
10፥13 ዘጸ1፥6
10፥14 ዘኍ1፥7:52፤2፥3-9
10፥15 ዘሌ24፥11፤ዘኍ1፥8
10፥16 ዘኍ1፥9፤2፥7
10፥17 ቍ21፤ዘኍ4፥21-32
10፥18 ዘኍ1፥5፤2፥10-16

[8]“መለከቶቹን ካህናቱ የአሮን ልጆች ይንፉ፤ ይህም ለእናንተና ለሚመጡት ትውልድ የዘላለም ሥርዐት ይሁን:: [9]በገዛ ምድራችሁ በግፍ በመጣባችሁ ጠላት ላይ ስትዘምቱ መለከቶቹን ከፍ ባለ ድምፅ ንፉ፤ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) በአምላካችሁ (ኤሎሂም) ትታሰባላችሁ፤ ከጠላታችሁም እጅ ትድናላችሁ:: [10]እንዲሁም በደስታችሁ ቀናት ማለት በተደነገጉት በዓሎቻችሁና የወር መባቻ በዓል ስታከብሩ በሚቃጠል መሥዋዕታችሁና በኅብረት መሥዋዕታችሁ[1] ላይ መለከቱን ንፉ፤ እነዚህም በአምላካችሁ (ኤሎሂም) ፊት መታሰቢያ ይሆኑላችኋል:: እኔ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) አምላካችሁ (ኤሎሂም) ነኝ::”

## እስራኤላውያን ከሲና ተነሡ

[11]በሁለተኛው ዓመት፣ ሁለተኛው ወር በገባ በሃያኛው ቀን ደመናው ከምስክሩ ማደሪያ ላይ ተነሣ:: [12]ከዚያም እስራኤላውያን ከሲና ምድረ በዳ ተነሥተው ደመናው በፋራን ምድረ በዳ እስከከየረፍ ድረስ ከአንዱ ቦታ ወደ ሌላው ቦታ ተጓዙ:: [13]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሙሴ አማካይነት በሰጠው ትእዛዝ መሠረትም ለመጀመሪያ ጊዜ ተጓዙ::

[14]በመጀመሪያ የይሁዳ ሰፈር ሰራዊት በዐርማቸው ሥር ሆነው ተጓዙ፤ አለቃቸውም የአሚናዳብ ልጅ ነአሶን ነበር:: [15]የይሳኮር ነገድ ሰራዊት አለቃም የሰገር ልጅ ናትናኤል ነበር:: [16]እንዲሁም የዛብሎን ነገድ ሰራዊት አለቃ የኬሎን ልጅ ኤልያብ ነበር:: [17]ከዚህ በኋላ ማደሪያው ተነቀለ፤ ድንኳኑን የተሸከሙት ጌድሶናውያንና ሜራሪያውያንም ጕዞ ጀመሩ::

[18]ቀጥሎም የሮቤል ሰፈር ሰራዊት በዐርማቸው ሥር ሆነው ተጓዙ፤ አለቃቸውም

[1] 10 በተለምዶ የድነት መሥዋዕት ማለት ነው

9፥23 *የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ይጠብቁ ነበር*፡ በቍ 15-23 ያለው የተደጋገመ ሐሳብ፣ እስራኤል በምድረ በዳ ጕዞው እግዚአብሔር ለሚሰጠው ምሪት ዘወትር በፍጹም መታዘዝ እንዳለበት ያመለክታል:: የእግዚአብሔር ትእዛዝ የሚከናወነው በሙሴ አማካይነት እንደ መሆኑ እዚህ ላይ ሙሴን መጥቀሱ ሚዛን ለመጠበቅ ነው፤ ደመናው ሲንቀሳቀስ ሕዝቡ እንዲጓዝ ምልክት እንደ ሆነ የሚተረጕም የእግዚአብሔር ወኪል ሙሴ ነበር:: ካለመታዘዛቸው የተነሣ የሚደርሰው አሳዛኝ ሁኔታ (ም 11) በዚህ አንቀጽ ውስጥ ካለው መታዘዝ አንጻር ሲታይ ዐመፃቸው ያመዝናል::

10፥2 *መለከት*፤ ረጅም፣ ቀጥ ያለና ቀጭን ሆኖ ከመጨረሻው በኩል ሰፋ ያለ አፍ ያለው የሚነፋ ውስጠ ክፍት የከብት ቀንድ፣ ከብረታ ብረት ወይም ከሌላ የሚሠራ ትእዛዝ ለማስተላለፍ፣ ዐዋጅ ለመንገር፣ ለዝማሬ አገልግሎት ይውላል::

10፥3 *ሲነፉ*፤ ለመሰብሰብ ብቻ ሳይሆን ለጕዞ (ቍ 5-6)፣ ለጦርነትና (ቍ 9) በዓልን ለማክበር (ቍ 10) ጥሪ ለማስተላለፍ ያገለግሉ ነበር:: ለተለያዩ የድምፀት ምልክቶች ጥቅም ላይ በመዋላቸው (ቍ 7) መለከት ነፊ የካህናት ቡድን ተቋቋመ (ቍ 8):: በኢያሪኮ ጦርነት ጊዜ ከበግ ቀንድ ስለ ተሠሩ ስለ ሰባት ቀንደ መለከቶች አገልግሎት ለመረዳት ኢሱ 6፥4 ይመ::

10፥10 *በ ... በዓሎቻችሁ ... መለከቱን ንፉ*፤ የመለከቱ ድምፅ እንደ መግቢያ በመሆን ሕዝቡ ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት እንዲፈጥር ያዘጋጅ ነበር:: ኋላም ለእግዚአብሔር በሚቀርበው አምልኮ የመዘምራን ኅብረት እንዲያገለግሉበት ዳዊት የተለያዩ የሙዚቃ መሣሪያዎች እንዲጨመሩ በማድረግ ሙሉ በሙሉ አደራጀ (1ዜና 25 ይመ)፤ ይሁን እንጂ ከብር የተሠሩ መለከቶች በእግዚአብሔር ቃል ኪዳን ታቦት ፊት ዘወትር እንዲነፉ አድርጎአል (1ዜና 16፥6)::

*10፥11-28*፤ የዚህ ክፍል አወቃቀር ቀጥሎ ተመልክቶአል፤ (1) ቍ 11 ድርጊቱ የተፈጸመበት ጊዜ፤ (2) ቍ 12-13 ስለ ጕዞው አጠር ያለ መግቢያ፤ (3) ቍ14-17 በይሁዳ የሚመሩ ነገዶች ጕዞ መጀመራቸው (2፥3-9 ይመ)፤ (4) ቍ 18-21 በሮቤል የሚመሩ ነገዶች ጕዞ መጀመራቸው (2፥10-16 ይመ)፤ (5) ቍ 22-24 በኤፍሬም የሚመሩ ነገዶች ጕዞ መጀመራቸው (2፥18-24 ይመ)፤ (6) ቍ 25-27 በዳን የሚመሩ ነገዶች ጕዞ መጀመራቸው (2፥25-31 ይመ)፤ (7) ቍ 28 ስለ ጕዞው አሰላለፍ የማጠቃለያ ሐሳብ::

10፥11 *ሁለተኛው ወር በገባ በሃያኛው ቀን*፤ ሕዝቡ በሲና ተራራ አካባቢ ዐሥራ አንድ ወራት ከቈየ በኋላ በደመና እየተመራ ወደ ተስፋዪቱ ምድር ጕዞ ጀመረ:: በዘኍልቍ መጽሐፍ ሁለተኛው ትልቁ ክፍል (10፥11-22፥1) ከዚህ ጥቅስ ይጀምራል:: እስራኤላውያን በጥቂት ወራት ውስጥ ከነዓንን ድል አድርገው ለመያዝ ከሚያስችላቸው ጕዞ ወደ ኋላ አሉ::

*10፥14-27*፤ የዐሥራ ሁለቱ ነገድ መሪዎች ስም ለአራተኛ ጊዜ በመጽሐፉ ውስጥ ተጠቅሶአል (1፥5-15፤ 2፥3-31፤ 7፥12-83 ይመ):: የጕዞው አሰላለፍ በም 2 ከተጠቀሰው ጋር በመሠረቱ ተመሳሳይ ነው:: አዲስ ነገር ቢኖር ማደሪያውን ድንኳን የተሸከሙ የጌድሶንና የሜራሪ ልጆች በይሁዳ የሚመራውን ሦስቱን ነገዶች መከተላቸው (ቍ 17) ንዋየ ቅዱሳቱን የሚሸከሙ ቀዓታውያን ደግሞ በሮቤል የሚመራውን ሦስቱን ነገዶች ተከትለው መጓዛቸው ነው (ቍ 21)::

10፥14 *በዐርማቸው*፤ በ2፥3:10:18:25 እንደ ተጠቀሰው አራቱም የሦስት የሦስት ነገድ ቡድኖች በአንድ ላይ ለመሰብሰብ ብና ለመደራጀት እያንዳንዱ የነገድ ቡድን ዐርማ ወይም ሰንደቅ ዐላማ ነበረው::

የሰዲዮር ልጅ ኤሊሱር ነበር። 19የስምዖን ነገድ ሰራዊት አለቃም የሱሪሰዳይ ልጅ ሰለሚኤል ነበር። 20እንዲሁም የጋድ ነገድ ሰራዊት አለቃ የራጉኤል ልጅ ኤሊሳፍ ነበር። 21ከዚህ በኋላ ቀዓታውያን ንዋያተ ቅዱሳቱን ተሸክመው ተጓዙ፤ እነርሱ ከመድረሳቸው በፊት ማደሪያው ተተክሎ ነበር።

22ቀጥሎም የኤፍሬም ሰፈር ሰራዊት በዐርማቸው ሥር ሆነው ተጓዙ፤ አለቃቸውም የዓሚሁድ ልጅ ኤሊሳማ ነበር። 23እንዲሁም የምናሴ ነገድ ሰራዊት አለቃ የፍዳሱር ልጅ ገማልኤል ነበር። 24የብንያም ነገድ ሰራዊት አለቃም የጋዴዮን ልጅ አቢዳን ነበር።

25በመጨረሻም የዳን ሰፈር ሰራዊት ለሁሉም ክፍሎች የኋላ ደጀን በመሆን በዐርማቸው ሥር ተጓዙ፤ አለቃቸውም የአሚሳዳይ ልጅ አኪዔዘር ነበር። 26እንዲሁም የአሴር ነገድ ሰራዊት አለቃ የኤክራን ልጅ ፋግኤል ነበር። 27እንዲሁም የንፍታሌም ነገድ ሰራዊት አለቃ የዔናን ልጅ አኪሬ ነበር። 28እንግዲህ የእስራኤል ሰራዊት የጕዞ አሰላለፍ ሥርዐት ይህ ነበር።

29በዚህ ጊዜ ሙሴ የሚስቱን አባት የምድያማዊውን የራጉኤልን ልጅ ኦባብን፣ "እነሆ፤ እግዚአብሔር፣ (ያህዌ) 'እሰጣችኋለሁ' ወዳለን ምድር ጕዞ ጀምረናል፤ በመልካም ሁኔታ ስለምናኖርህ ከእኛ ጋር ሂድ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ለእስራኤል በጎ ነገር ለማድረግ ቃል ገብቶአልና" አለው።

30እርሱም መልሶ፣ "ይህስ አይሆንም፤ አልሄድም፤ ወደ አገሬና ወደ ወገኖቼ ተመልሼ እሄዳለሁ" አለው።

31ሙሴ ግን እንዲህ አለ፤ "እባክህ አትለየን፤ በምድር በዳ ውስጥ የት መስፈር እንደሚገባን አንተ ታውቃለህ፤ ዐይናችንም ትሆናለህ። 32ከእኛ ጋር ብትሄድ እግዚአብሔር (ያህዌ) ከሚያደርግልን መልካም ነገር ሁሉ እኛም እናደርግልሃለን።"

33ስለዚህ ከእግዚአብሔር (ያህዌ) ተራራ ተነሥተው የሦስት ቀን መንገድ ተጓዙ፤ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ቃል ኪዳን ታቦትም በእነዚያ ሦስት ቀናት ውስጥ የሚያርፉበትን ቦታ በመፈለግ ፊት ፊታቸው ይሄድ ነበር። 34ከሰፈራቸው በሚነሡበት ጊዜ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ደመና ቀን ቀን ከላያቸው ነበር።

35ታቦቱ ለጕዞ በተነሣ ጊዜ ሁሉ ሙሴ፣
"እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤ ተነሥ!
ጠላቶችህ ይበተኑ፤
የሚጠሉህም ከፊትህ ይሽሹ" ይል ነበር።

36ባረፈ ጊዜም፣
"እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤
በብዙ ሺህ ወደሚቈጠሩት
እስራኤላውያን ተመለስ" ይል ነበር።

### ከእግዚአብሔር የወረደ እሳት

11 በዚህ ጊዜ ሕዝቡ ስለ ደረሰባቸው ችግር በእግዚአብሔር (ያህዌ) ላይ አጕረመረሙ፤ እግዚአብሔርም (ያህዌ) ማጕረምረማቸውን በሰማ ጊዜ በጣም ተቈጣ፤ ከዚያም የእግዚአብሔር (ያህዌ) እሳት በመካከላቸው ነደደች፤ ከሰፈሩም ዳርቻ ጥቂቱን በላች። 2ሕዝቡ ወደ ሙሴ ጮኹ፤ ሙሴም ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጸለየ፤ እሳቲቱም ጠፋች። 3ከዚህ የተነሣም የቦታው ስም፣ "ተቤራ"[3] ተባለ፤ የእግዚአብሔር (ያህዌ) እሳት በመካከላቸው ነዳለችና።

### እግዚአብሔር ለእስራኤላውያን የላከላቸው ድርጭት

4ድብልቅ ሕዝብ ሌላ ምግብ ጐመጀ፤ እስራኤላውያንም እንዲህ እያሉ ያጕረመርሙ ጀመር፤ "ምነው የምንበላው ሥጋ ባገኘን ኖሮ! 5በግብፅ ያለምንም ዋጋ የበላነው ዓሣ እንዲሁም ዱባው፣ በጢኹ፣ ኩራቱ፣ ነጭ ሽንኩርቱ ትዝ ይለናል። 6አሁን ግን የምግብ ፍላጎታችን ጠፍቶአል፤ ከዚህ መና በስተቀር የምናየው የለም!"

7መናው እንደ ድንብላል ዘር ትንንሽ ሆኖ የሙጫ መልክ ነበረው። 8ሕዝቡ ተዘዋውሮ

10፥19 ዘኍ1፥6
10፥20 ዘኍ1፥14
10፥21 ቍ17፤ ዘኍ2፥17፤4፥20
10፥22 ዘኍ1፥10፤ 2፥24
10፥23 ዘኍ1፥10
10፥24 ዘኍ1፥11
10፥25 ዘኍ1፥12፤ 2፥31
10፥26 ዘኍ1፥13
10፥27 ዘኍ1፥15
10፥29 ዘፍ12፥7፤ 15፥14፤ዘፀ2፥18፤ 3፥1፤መሳ4፥11
10፥30 ዘፀ18፥27፤ ማቴ21፥29
10፥31 ኢዮ29፥15
10፥32 ዘፀ12፥48፤ ዘዳ10፥18፤መዝ22፥ 27-31፤67፥5-7
10፥33 ቍ12፤ ዘዳ1፥33፤10፥8፤31፥9 ፤ኢሱ3፥3፤መሳ20፥ 27፤2ሳሙ15፥24፤ ኤር31፥2
10፥34 ዘኍ9፥15-23
10፥35 ዘዳ5፥9፤ 7፥10፤32፥41፤መሳ5፥ 31፤ሳሙ2፥1፤2ዜና6፥ 41፤መዝ17፥13፤44፥ 26፤68፥1፤2፥9፤92፤94 ፥2፤132፥8፤ኢሳ 17፥12-14፤59፥18
10፥36 ዘፍ15፥5፤ 26፥4፤ዘዳ1፥10፤10፥ 22፤ነህ 9፥23፤ኢሳ 52፥8፤63፥17
11፥1 ዘፀ4፥14፤14፥ 11፤16፥7፤ዘሌ10፥2፤ ዘኍ12፥2፤21፥28፤ዘዳ 1፥34፤መዝ፤78፤63፤ ኢሳ26፥11፤ሰቆ3፥39
11፥2 ዘፍ20፥7፤ ዘኍ21፥7፤ዘዳ9፥19፡20፤ 1ሳሙ2፥25፤12፥23፤ መዝ106፥23፤ዮና2፥1
11፥3 ዘዳ9፥22፤ ዘኍ16፥35፤ኢዮ 1፥16፤ኢሳ10፥17
11፥4 ቍ18፤ዘፀ16፥3
11፥5 ዘፀ16፥3፤ ዘኍ21፥5
11፥6 ዘፀ16፥14

11፥7 ዘፍ2፥12፤ዘፀ16፥31

[3] ተቤራ ማለት ማቃጠል ማለት ነው

10፥29 *የራጉኤልን ልጅ ኦባብን፤* አባብ የሙሴ ሚስት ወንድም የነበረ ነው። *ራጉኤል፤* ዮቶር የተባለው ነው (ዘፀ 2፥18፤ 3፥1 ይመ)።

10፥31 *ዐይናችንም ትሆናለህ* አባብ ሙሴ ላቀረበው ልመና እሺ ማለቱ በመሳ 1፥16 ላይ ተጠቅሶአል።

10፥33 *የሦስት ቀን፤* የእስራኤል ነገዶች ከፍተኛ ቍጥር ያለውን ሕዝብ ያቀፉ በመሆናቸውና በዚህ መልክ ተደራጅተው ሲጓዙ የመጀመሪያ ጊዜአቸውም ስለ ሆነ በመጀመሪያው ጕዞአቸው ብዙ ርቀው እንዳልሄዱ መገመት ይቻላል።

*10፥35-36፤* እስራኤል በእግዚአብሔር አዝማችነት ለሰልፍ የወጣ የእግዚአብሔር ሰራዊት ከሲና እስከ ኢየሩሳሌም ድረስ በድል የተጠናቀቀውን የእግዚአብሔርን ሰልፍ በማወደስ የተጻፈው መዝሙር የመክፈቻ ቃላት ሆኖአል (መዝ 68፥1 ይመ)።

11፥1 *ሕዝቡ ... አጕረመረሙ፤* ሙሴና የእስራኤል ሕዝብ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ሙሉ በሙሉ መቀበላቸውና ማድረጋቸው በዚህ መጽሐፍ በመጀመሪያዎቹ ዐሥር ምዕራፎች ውስጥ ተደጋግሞ በአጽንዖት ተገልጾአል። ነገር ግን ሦስት ቀን ብቻ ከተጓዙ በኋላ ሕዝቡ በታማኝነት ሳይቈይ ወደ ማጕረምረም ሲመለስ ይታያል። ከአንድ ዓመት በፊት፣ ከግብፅ ባርነት ነጻ ወጥተው ቀይ ባሕርን ከተሻገሩ ከሦስት ቀን በኋላ እንደዚሁ ዐይነት ጕርምርምታ አሰምተው ነበር (ዘፀ 15፥22-27)፤ ከዚህ በኋላ ስለ መና (ዘፀ 16) እንዲሁም ውሃ ስላጡ አጕረምርመው ነበር (ዘፀ 17፥1-7)። *የእግዚአብሔር እሳት፤* ይህ የሚያጠራ እሳት ከሰፈሩ ዳርቻ ወደ ሰፈሩ መኻል እንዳይገባ የእግዚአብሔር ምሕረት ተቈጣጥሮት ነበር።

11፥3 *ተቤራ፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ።

11፥4 *ድብልቅ ሕዝብ፤* እስራኤላውያን ከግብፅ ሲወጡ ተከትለዋቸው የወጡትን ከእስራኤል ወገን ያልሆኑትን ሕዝቦች የሚያመለክት ነው፤ እነዚህ በተደጋጋሚ በእስራኤል ሰፈር ለተፈጠረው ጕርምርምታና ችግር ምክንያት ነበሩ። እግዚአብሔርንና ምሕረቱን የማያውቁት እነዚህ ሰዎች፣ እግዚአብሔርን ያወቁትን እስራኤላውያንን በእግዚአብሔር ላይ እንዲያምፁ ገፋፉአቸው። *የምንበላው ሥጋ ባገኘን ኖሮ!* በዘፀ 16 ላይ እንዳደረጉት ሁሉ ሕዝቡ እግዚአብሔር ያደረገላቸውን ነገር በመርሳት ስለሚበሉት ምግብ ማጕረምረም ጀመሩ (መዝ 106፥14 ይመ)። በግብፅ አገር በባርነት በኖሩበት ዘመን ሥጋ የተለመደ ምግባቸው እንዳልነበረ ግልጽ ነው፤ አሁን አዲስ መከራ ውስጥ ገብተው የቀድሞውን ችግር እንደ ቀላል በመቍጠር ያለፈውን ጊዜ ማድነቅ ጀመሩ።

11፥5 *ዓሣ... ዱባው... ነጭ ሽንኩርቱ፤* በምድረ በዳ ይበሉት ከነበረው መና ጋር ሲነጻጸር በግብፅ ብዙ የምግብ ዐይነት እንደ ነበር ያመለክታል።

11፥7 *መና፤* ሰዎች ስለ መና የተለያዩ አስተያየቶችን

በመልቀም በወፍጮ ከፈጨ ወይም በሙቀጫ ከወቀጠ በኋላ በምንቸት ይቀቅለው ወይም ይጋግረው ነበር፤ ጣዕሙም በወይራ ዘይት የተጋገረ ያህል ይጣፍጥ ነበር። [9]ጤዛው ሌሊት በሰፈር ላይ በሚወርድበት ጊዜ መናውም እንዲሁ ይወርድ ነበር።

[10]ሙሴ፣ ሕዝቡ ሁሉ በየቤተ ሰቡ፣ በየድንኳኑ ደጃፍ ሆኖ ሲያለቅስ ሰማ። *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) እጅግ ተቈጣ፤ ሙሴም ተጨነቀ። [11]እርሱም *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ “እንዲህ ያለውን መከራ በባሪያህ ላይ ለምን አመጣህ? የዚህን ሕዝብ ሁሉ ሸክም የጫንህብኝስ ምን አስቀይሜህ ነው? [12]ይህን ሁሉ ሕዝብ የፀነስሁት እኔ ነኝን? እኔስ ወለድሁትን? ታዲያ ሞግዚት ሕፃን እንደምትታቀፍ በክንዴ ታቅፌ ለቀድሞ አባቶቻቸው ትሰጣቸው ዘንድ በመሐላ ቃል ወደ ገባህላቸው ምድር እንዳስገባቸው የምትነግረኝ ለምንድነው? [13]ለዚህ ሁሉ ሕዝብስ ሥጋ ከወዴት አመጣለሁ? ሁሉም ‘የምንበላው ሥጋ ስጠን’ እያሉ ያለቅሱብኛል። [14]እጅግ ከብዶኛልና ይህን ሁሉ ሕዝብ ብቻዬን ልሸከም አልችልም። [15]እንዲህስ ከምታደርገኝ በፊትህ ሞገስ አግኝቼ እንደ ሆነ አሁኑኑ ግደለኝ፤ የሚደርስብኝን ጥፋት አልይ።”

[16]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ “በሕዝቡ መካከል በመሪነትና በአለቅና ብቃት አላቸው የምትላቸውን ሰባ የእስራኤል ሽማግሌዎች አምጣልኝ፤ ካንተም ጋር ይቆሙ ዘንድ ወደ መገናኛው ድንኳን እንዲመጡ አድርግ። [17]ወደዚያም ወርጄ አነጋግርሃለሁ፤ ባንተ ላይ ካለው መንፈስ ወስጄ በእነርሱ ላይ አደርጋለሁ፤ የሕዝቡንም ሸክም ብቻህን እንዳትሸከም እነርሱ ያግዙሃል።

[18]“ለሕዝቡ እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ ‘ነገ ሥጋ ትበላላችሁና ራሳችሁን በመቀደስ ተዘጋጁ’። “በግብፅ ተመችቶን ነበር፤ አሁን ግን ሥጋ ማን ይሰጠናል!” ብላችሁ ያለቀሳችሁትን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሰምቶአል፤ ስለዚህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሥጋ ይሰጣችኋል፤ እናንተም ትበላላችሁ። [19]የምትበሉትም ለአንድ ወይም ለሁለት ቀን ወይም ለአምስት፣ ለዐሥር ወይም ለሃያ ቀን አይደለም፤ [20]ነገር ግን በአፍንጫችሁ እስኪወጣና እስኪያንገፈግፋችሁ ድረስ ወር ሙሉ ትበሉታላችሁ፤ በመካከላችሁ ያለውን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ንቃችሁ በፊቱ፣ “ለምን ከግብፅ ወጣን?” ብላችሁ አልቅሳችኋልና።”

[21]ሙሴ ግን እንዲህ አለ፤ “እነሆ እኔ በስድስት መቶ ሺህ እግረኛ መካከል እገኛለሁ፤ አንተ ደግሞ ‘ወር ሙሉ የሚበሉትን ሥጋ እኔ እሰጣቸዋለሁ!’ ብለሃል፤ [22]ታዲያ ስንት የበግ፣ የፍየልና የከብት መንጋ ቢታረድላቸው ይበቃ ይሆን? በባሕር ያለው ዓሣ ሁሉ ቢያዝ ሊዳረሳቸው ይችላልን?”

[23]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ለሙሴ፣ “በውኑ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ክንድ ይህን ያህል አጭር ነውን? የነገርሁህ ቃል እውነት መሆን አለመሆኑን አሁኑኑ ታየዋለህ” ሲል መለሰለት።

11፥8 ዘፀ16፥16
11፥9 ዘፀ16፥13
11፥10 ቍ4
11፥11 ዘዳ34፥30፤ ዘፀ5፥22፤18፥18
11፥12 ዘዳ12፥7፤ ዘፀ13፥5፤ዘኍ14፥16፤ ኢሳ40፥11፤49፥23፤ 66፥11፡12
11፥13 ዘፀ12፥37፤ ዮሐ6፥5-9
11፥14 ዘፀ18፥18
11፥15 ዘፀ32፥32፤ 1ነገ19፥4፤ኢዮ6፥9፤ 7፥15-16፤9፥21፤ 10፥1፤ኢሳ38፥12፤ ዮና4፥3
11፥16 ዘፀ3፥16፤ 18፥25፤40፥2
11፥17 ቍ25፡29፤ ዘፀ18፥18፤19፥20፤ 1ሳሙ10፥6፤2ነገ2፥9፡ 15፤3፥12፤ኢሳ32፥15፤ 40፥5፤63፥11፤ኤር19 ፥1፤ኢል 2፥28፤ሐጌ 2፥5
11፥18 ዘፀ16፥7፤ 19፥10፤መዝ78፥20፤ ሐሥ7፥39
11፥20 ቍ33፤ ዘሌ26፥43፤ኢሱ24፥ 27፤መሳ8፥23፤1ሳሙ 10፥19፤ኢዮ20፥13፡ 23፤31፥28፤መዝ78፥ 29፤106፥14፡15፤ኢሳ 59፥13፤ሆሴ13፥11
11፥21 ዘፀ12፥37
11፥22 ማቴ15፥33
11፥23 ዘኍ23፥19፤ 1ሳሙ15፥29፤ኢሳ 50፥2፤59፥1፤ሕዝ 12፥25፤24፥14

ሰንዝረዋል፤ ለምሳሌ አንዳንዶች ወደ ሰኔ መጀመሪያ ላይ በሲና አካባቢ የሚገኙ የተለያየ መጠን ያላቸው ነፍሳት ከውስጣቸው የሚያወጡት ፈሳሽ ሲነፍስበት ፈጥኖ ጠጣር የሚሆንና የማጣበቅም ጠባይ ያለው ሙጫ ነው ይላሉ። ነገር ግን በተፈጥሮ ከሚገኙት ነገሮች በክፍሉ የተጠቀሱትን መስፈርት የሚያሟላ የለም። ይልቁን መና እግዚአብሔር በምድረ በዳ ለሕዝቡ የሰጠው ልዩ ምግብ እንደ ሆነ ብዙ መረጃዎች ያመለክታሉ፤ (1) ለመና የገባው የዕብራይስጡ ቃል ትርጒም በዘመኑ በሕዝቡ ዘንድ የተለመደ እንዳልነበረ ያመለክታል (ዘፀ 16፥ 31 ይመ)፤ (2) በሌላ ጊዜ በሌሎች ሰዎች ዘንድ የተለመደ ምግብ እንዳልነበረ የመናው መልክና ጣዕም ያመለክታል (ዘፀ 16፥31)፤ (3) መናው በየቀኑ በብዛት መውረዱና ሳይቋረጥ መገኘቱ በተለይ በስድስተኛው ቀን መጠኑ ዕጥፍ መሆኑና በሰባተኛው ቀን ምንም ያለመውረዱ (ዘፀ 16፥22፡27)፣ ከተፈጥሮ ክሥተት ጋር አንድ ነው ለማለት ያስቸግራል፤ (4) ሰዎቹ የትም ይሁኑ መናው በምድረ በዳው ጕዞአቸው ወቅት ሁሉ ተትረፍርፎ ሊገኝ መቻሉ (ዘፀ 16፥35) በተፈጥሮ ከሚገኝ ነገር ጋር ይቃረናል፤ (5) ለመጪው ትውልድ ምስክር ይሆን ዘንድ በታቦቱ ፊት ለዐይነት የሚሆን መና ለወደ ፊት እንዲቈይ መደረጉ (ዘፀ 16፥33-34)፣ የተለየ ምግብ እንደ ነበር ያመለክታል።

11፥10 *እግዚአብሔርም እጅግ ተቈጣ*፤ “ከሰማይ እንጀራ አዘንብላችኋለሁ” (ዘፀ 16፥4)፣ የከበረውን የእርሱን ስጦታ ማቃለላቸው እግዚአብሔርን አስቈጣው። ሕዝቡ መናውን ከተቀበለ በኋላ መታዘዝ አለመታዘዙ የሚታይበት ልዩ መፈተኛ እንደ ሆነ እግዚአብሔር ተናግሮ ነበር (ዘፀ 16፥4)። እግዚአብሔር ወደ ፊት ሊሰጣቸው ካሰበው በረከት አኳያ (10፥32)፣ ሕዝቡ በየቀኑ የሚያገኙትን መና የቸሩ እግዚአብሔር በጎ ስጦታና ሊመጣ ላለው ታላቅ በረከት ተስፋ መሆኑን ዐውቀው ያለ ማንጐራጐር መቀበል ነበረባቸው። መናውን ማጣጣላቸው እግዚአብሔርን እንደ ማቃለል ነው። እምነታቸውም ተፈትኖ አላለፈም። *ሙሴም ተጨነቀ*፤ ሕዝቡ ከእግዚአብሔር ለተሰጣቸው መና የነበራቸው ግምት ሙሴንም ጭምር አውኮታል። የማጕረምረማቸው ፍሬ ነገር ምን እንደ ሆነ እግዚአብሔርን በመጠየቅ ፈንታ ሙሴ እንዲህ ያለው ውሌታ ቢስ ሕዝብ በእርሱ ይመራ ዘንድ ለምን እንደ ተሰጠው ጠየቀ።

*11፥11-15፤* ጥድፊያ፣ ምፀትና ብርቱ ስሜት የሞላበት የጭንቀትና የማጕረምረም ጸሎት ነው።

11፥12 *ይህን ሁሉ ሕዝብ የፀነስሁት እኔ ነኝን?* ሕዝቡን የፀነሰውና ተንከባክቦ የሚይዛቸው የተስፋ ቃል የሰጣቸው እግዚአብሔር መሆኑን የሚያመለክት አባባል ነው። “እጅግ ከብዶኛል” (ቍ 14፤ ከኤልያስ ጋር ያነጻጽሩ፣ 1ነገ 19) በማለት ሙሴ በሕዝቡና በእግዚአብሔር መካከል የመቆሙን ተግባር ለመልቀቅ ጥያቄ ያቀርባል። የሕዝቡን ማጕረምረም ዘወትር ከመስማት ይልቅ ሙሴ ሞት እንደሚሻል አረጋግጦ ይናገራል (ቍ 15)።

*11፥16-34፤* እግዚአብሔር የራሱ ነቢይ እጅግ በተጨነቀ ጊዜ ምሕረትና መርገም አዘል የሆነ ሁለት ዐይነት መልስ ሰጥቶታል፤ (1) አሁን የሙሴን የኀላፊነት ሸክም የሚጋሩ ሰባ መሪዎች በመመረጣቸው (ቍ 16-17) ለሙሴ ምሕረት ሆኖለታል፤ (2) ለማጕረምረማቸው ተመጣጣኝ የሆነ ርግማን በሕዝቡ ላይ ደርሶአል፤ ሥጋ ለመኑ፤ በሥጋ ታመሙ (ቍ 18-34)።

11፥18 *ሥጋ ትበላላችሁ*፤ በየቀኑ ከመናው በስተቀር ሌላ ምግብ ባለማግኘታቸው ያደረባቸው ጭንቀት ሕዝቡ የእግዚአብሔርን በጎነት እንዲፈታተኑ አደረጋቸው። ሥጋ ጐምጅተው እጅግ አንጐራጐሩ። ስለዚህ እስከሚታመሙና እስከሚሰለቻቸው ድረስ (ቍ 20) መብላት የቻሉትን ያህል እንዲበሉ ሥጋ ተሰጣቸው።

11፥20 *እግዚአብሔርን ንቃችሁ*፤ የሕዝቡ ዐቢይ ችግር ሥጋ ያለ ማግኘታቸው ሳይሆን፣ በመካከላቸው ያለውንና ለሚፈልጉት መልካም ነገር ሁሉ ምንጭ ለሆነው ለእግዚአብሔር የሚገባውን ምስጋናና ክብር አለመስጠታቸው ነው።

11፥21 *በስድስት መቶ ሺህ እግረኛ፤* ቍጥሩ ቋሚ ነው፤ ብዛቱ ይህን የሚያህል ተዋጊ ሰራዊት መኖሩ የጠቅላላው ሕዝብ ቍጥር ከሁለት ሚሊዮን በላይ እንደ ሆነ ያመለክታል (የ1፥46 ማብ ይመ)። ይህን ቍጥሩ እጅግ ከፍተኛ የሆነ ሕዝብ ሥጋ የማብላቱ ጕዳይ ሙሴን ያስጨነቀው ነገሩ የማይቻልና ቀልድ መስሎ ስለታየው ነው።

11፥23 *በውኑ የእግዚአብሔር ክንድ ይህን ያህል አጭር ነውን?* ለሰው የማይቻለው ሁኔታ እግዚአብሔር የኀይሉን ታላቅ

[24]ሙሴም ወጣና *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ያለውን ለሕዝቡ ነገራቸው፤ ከሕዝቡም ሽማግሌዎች ሰባውን ሰብስቦ በድንኳኑ ዙሪያ እንዲቆሙ አደረጋቸው። [25]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በደመና ወርዶ ተናገረው፤ በሙሴ ላይ ከነበረውም መንፈስ ወስዶ በሰባው ሽማግሌዎች ላይ አሳደረባቸው፤ መንፈሱ ባደረባቸውም ጊዜ ትንቢት ተናገሩ፤ ከዚያ በኋላ ግን አልደገሙትም።[ፕ]

[26]ኤልዳድና ሞዳድ የተባሉ ሁለት ሰዎች ግን ሰፈር ውስጥ ቀርተው ነበር፤ እነርሱም ከሽማግሌዎቹ ጋር ተቈጥረው ሳለ ወደ ድንኳኑ አልሄዱም ነበር፤ ሆኖም የእግዚአብሔር መንፈስ በእነርሱም ላይ ስላደረባቸው ሰፈር ውስጥ እያሉ ትንቢት ተናገሩ። [27]አንድ ወጣትም ሮጦ በመሄድ፣ "ኤልዳድና ሞዳድ ሰፈር ውስጥ ትንቢት ይናገራሉ" ብሎ ለሙሴ ነገረው።

[28]ከወጣትነቱ ጀምሮ የሙሴ ረዳት የነበረው የነዌ ልጅ ኢያሱም ተነሥቶ፣ "ጌታዬ ሙሴ ሆይ፤ ከልክላቸው እንጂ!" ሲል ተናገረ።

[29]ሙሴ ግን መልሶ፣ "ስለ እኔ ተቈርቍረህ ነውን? *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ሕዝብ ሁሉ ነቢያት ቢሆኑ፣ *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) መንፈሱን ቢያሳድርባቸው ምንኛ ደስ ባለኝ!" አለ፤ [30]ከዚያም ሙሴና የእስራኤል ሽማግሌዎች ወደ ሰፈር ተመለሱ።

[31]በዚህ ጊዜ ነፋስ *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘንድ ወጥቶ ድርጭቶችን ከባሕር ወደ ሰፈር አመጣ፤ በየአቅጣጫውም ከፍታው ሁለት ክንድ፣[ሉ] ርቀቱም የአንድ ቀን መንገድ ያህል እስኪሆን ድረስ በሰፈሩ ዙሪያ ከመራቸው፤ [32]በዚያን ዕለት ቀንና ሌሊቱን በሙሉ፣ በማግሥቱም ሙሉውን ቀን እንደዚሁ ሕዝቡ ወጥቶ ድርጭቶች ሰበሰበ፤ ከዐሥር የቆሮስ[ከ] መስፈሪያ ያነሰ የሰበሰበ ማንም አልነበረም፤ የሰበሰቡትንም በሰፈሩ ዙሪያ ሁሉ አሰጡት። [33]ነገር ግን ሥጋው ገና በጥርስና በጥርሳቸው መካከል ሳለ አላምጠው ሳይውጡት *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ቍጣ በላያቸው ነደደ፤ እግዚአብሔርም ሕዝቡን በታላቅ መቅሠፍት ክፉኛ መታ። [34]ሌላ ምግብ ለማግኘት የጐመጁትን ሰዎች በዚያ ስለ ቀበሩአቸው የቦታው ስም "ቂብሮት ሃታአባ"[ፐ] ተባለ።

[35]ሕዝቡም ከቂብሮት ሃታአባ ወደ ሐጼሮት ተጕዘው እዚያው ሰፈሩ።

11፥25 ቍ17:26፡ 29፤ዘፀ19፥9፤ዘኍ12፥5፤24፥2፤መሳ3፥10፤ 1ሳሙ10፥6:10፤ 19፥20፤23፤2ዜና 15፥1፤ሐሥ2፥17
11፥26 ቍ25፤1ዜና 12፥18፤ራእ1፥10
11፥28 ዘፀ17፥9፤ 33፥11፤ዘኍ13፥8፤26 ፥65፤ኢያ1፥1፤14፥ 10፤ ማር9፥38-40
11፥29 ቍ17፤ዘኍ 27፥18፤1ሳሙ10፥5፤ 19፥20፤2ዜና24፥19፤ ኤር7፥25፤44፥4፤ 1ቆሮ14፥5
11፥31 ዘፀ16፥13፤ መዝ78፥26-28
11፥33 ቍ18-20፤ ዘኍ14፥18፤ዘዳ 9፥7፤ መሳ2፥12መዝ78፥30 ፤106፥15:29፤2ነገ22፥ 17፤ኢሳ10፥16፤ኤር 44፥3፤ሕዝ8፥17
11፥34 ዘኍ33፥16፤ ዘዳ9፥22
11፥35 ዘኍ33፥17
12፥1 ዘፀ15፥20፤ 2፥21
12፥2 ዘኍ16፥3፤ 11፥1
12፥3 ማቴ11፥29
12፥5 ዘፀ13፥21፤ ዘኍ11፥25
12፥6 ዘፍ15፥1፤ 20፥3፤1ሳሙ3፥7:21፤ 20፥3፤ማቴ27፥19፤ ዕብ1፥1

## ማርያምና አሮን ሙሴን ተቃወሙ

**12** ሙሴ ኢትዮጵያዊት ሴት አግብቶ ነበርና ባገባት ኢትዮጵያዊት ምክንያት ማርያምና አሮን ይነቅፉት ጀመር። [2]እነርሱም፣ "*ለመሆኑ እግዚአብሔር* (ያህዌ) የተናገረው በሙሴ አማካይነት ብቻ ነውን? በእኛስ አልተናገረም?" ተባባሉ፤ *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ይህን ሰማ።

[3]ሙሴ በምድር ላይ ካሉት ሰዎች ሁሉ ይልቅ እጅግ ትሑት ሰው ነበር።

[4]ወዲያው *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን፣ አሮንንና ማርያምን፣ "ሦስታችሁም ውጡና ወደ መገናኛው ድንኳን ኑ" አላቸው፤ ሦስቱም ወጥተው ሄዱ። [5]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በደመና ዐምድ ወረደ፤ በድንኳኑም ደጃፍ ቆሞ አሮንንና ማርያምን ጠራቸው፤ ሁለቱም ወደ እርሱ በቀረቡ ጊዜ፣ [6]እንዲህ አላቸው፤ "ቃሌን አድምጡ፤

"*የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ነቢይ በመካከላችሁ ቢኖር፣
በራእይ እገለጥለታለሁ፤
በሕልምም እናገረዋለሁ።

[ፕ]25 *ትንቢት ተናገሩ፤ ከዚያ በኋላም ትንቢት መናገራቸውን አላቆሙም* የሚሉ አሉ። [ሉ]31 አንድ ሜትር ያህል ነው። [ፐ]34 የምኞት መቃብር ማለት ነው።

ነት የሚገልጽበት አጋጣሚ ነው።

11፥25 *ትንቢት ተናገሩ፤* 1ሳሙ 10፥5-6፤ 18፥10፤ 19፥20-24፤ 1ነገ 18፥29 ይመ። *ከዚያ በኋላ ግን አልደገሙትም፤* ለእነዚህ ሽማግሌዎች ጊዜያዊ የሆነ የትንቢት ስጦታ መሰጠቱ በመንፈስ ቅዱስ የተሾሙ ብቁ መሪዎች መሆናቸውን ለማጽናት ይመስላል።

11፥29 *ስለ እኔ ተቈርቍረህ ነውን?* እዚህ ላይ ሙሴ ምን ዐይነት ሰው እንደ ሆነ በግልጽ ይታያል። በኤልዳድና በሞዳድ ላይ በግልጽ በታየው የመንፈስ ቅዱስ ስጦታ በመከፋት ፈንታ ሙሴ የእግዚአብሔር ሕዝብ ሁሉ የመንፈስ ቅዱስ ስጦታ ቢቀበል ምኞቱ እንደ ሆነ ይገልጻል (ከፊል 1፥15-18 ጋር ያነጻጽሩ)። የሙሴን መሪነት በማቃለል በም 12 ላይ ለሚከሠተው ተቃውሞ ይህ ጥቅስ ተስማሚ መግቢያ ነው።

*11፥31-32፤* ጌታ ኢየሱስ አምስት ሺህ ሰዎችን (ዮሐ 6፥5-13 እንዲሁም ማቴ 15፥29-39) በመመገብ ያደረገውን ታምራት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ። በእነዚያ ክፍሎች የሰዎቹ ምግብ መብላት የእግዚአብሔርን ቸርነት የሚገልጽ ሲሆን፣ በዚህኛው ክፍል ግን የእግዚአብሔርን ቍጣ ያመለክታል።

11፥34 *ቂብሮት ሃታአባ፤* የስሙ ትርጕም "የምኞት መቃብር" ማለት ነው። እግዚአብሔር በቸርነቱ የሰጣቸውን መና ያናናቁ ሰዎች የተቀበሩበትን ስፍራ የሚያመለክት ነው።

12፥1 *ባገባት ኢትዮጵያዊት ምክንያት፤* ኩሽ የካም የበኵር ልጅ ነበር፤ ካም በደቡብ የዐባይ ሸለቆ ወደ ደቡባዊው ጫፍ ክልል ይኖር የነበረ ሕዝቧ አባት ሲሆን፣ ይህም ሕዝብ በዕብራውያን ዘንድ ይታወቅ ነበር (ዘፍ 10፥6-7)። ይህ የኩሽ አገርም ኢትዮጵያ ተብሎ ይጠራ ነበር። እዚህ የተጠቀሰችውም የሙሴ ሚስት ሲፓራ ልትሆን ትችላለች (ዘፀ 2፥15-22)፤ የተናገሩት ስለ ሲፓራ ከሆነ፣ "ኢትዮጵያዊት" የሚለውን ቃል መጠቀማቸው ወገኖቿን ምድያማውያንን በንቀት መናገራቸውን የሚያመለክት ነው። ነገር ግን ሙሴ የመጀመሪያ ሚስቱ ከሞተች በኋላ ሌላ ሚስት ማግባቱን ሳያመለክት አይቀርም። አሮንና ማርያም ሙሴን የተቃወሙት በዚች ሴት ምክንያት መስሉ ቢታይም ዋና ምክንያታቸው ግን ሙሴ ከእግዚአብሔር ጋር በነበረው ልዩ ግንኙነትና የትንቢት ስጦታ በመቅናታቸው ነበር (ቍ 2)።

12፥2 *በሙሴ አማካይነት ብቻ ነውን?* በእርግጥ ተናግሮአል። ሙሴ፣ አሮንና ማርያም ለእስራኤል የተሰጡ የእግዚአብሔር ስጦታዎች እንደ ሆኑ ሚክ 6፥4 ይናገራል። ማርያምና አሮን ወንድማቸውን ለመቃወም ያነሣሣቸው ለሰባዎቹ (70) ሽማግሌዎች የተሰጠው የትንቢት ስጦታ (11፥24-30) ይመስላል።

*12፥3፤* በዚህ ጽሑፍ ላይ ያለው ሐሳብ በሙሴ ላይ የቀረበው ወቀሳ ተገቢ አለመሆኑን ምናልባትም እንጋቢ እንዲያውቀው በኋላ የተጨመረ ሊሆን ይችላል።

12፥4 *ወዲያው፤* የእግዚአብሔር መልስ ቅጽበታዊ መሆኑ ድንጋጤን ያስከትላል (ኢዮ 22፥10፤ ኢሳ 47፥11፤ ኤር 4፥20 ይመ)።

12፥5 *ወረደ፤* መለኮታዊ መገለጥን ለማመልከት ብዙ ጊዜ ጥቅም ላይ ውሎአል። በ11፥25 ላይ እግዚአብሔር በምሕረት ወረደ፤ እዚህ ላይና በዘፍ 11፥5 ላይ ግን በቍጣ ለመፍረድ ወረደ። እያንዳንዱ የእግዚአብሔር መገለጥ ኢየሱስ ጸጋንና ፍርድን ተሞልቶ በሥጋ የመገለጡ ነጸብራቅና ተስፋ ነው ማለት ይቻላል።

*12፥6-8፤* ይህ ክፍል በግጥም መልክ መቅረቡ የበለጠ ክብደት እንዲኖረው ያደርጋል፤ የግጥሙ ፍሬ ነገር ግልጽ ነው፤

[7]ለአገልጋዬ ሙሴ ግን እንዲህ አይደለም፤
እርሱ በቤቴ ሁሉ የታመነ ነው።
[8]እኔ ከእርሱ ጋር የምነጋገረው ፊት ለፊት
ነው፤
በግልጽ እንጂ በልዩ ዘይቤ አይደለም፤
እርሱ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) መልክ ያያል።
ታዲያ እናንተ አገልጋዬን ሙሴን
ትቃወሙ ዘንድ
ለምን አልፈራችሁም?"

[9]የእግዚአብሔር (ያህዌ) ቍጣ በላያቸው ነደደ፤ እርሱም ትቶአቸው ሄደ።

[10]ደመናው ከድንኳኑ ላይ በተነሣ ጊዜ፣ እነሆ፤ ማርያም በለምጽ* ተመታች፤ እንደ በረዶም ነጣች። አሮንም ወደ እርሷ ዘወር ሲል ለምጽ ወርሶአት አየ፤ [11]ሙሴንም እንዲህ አለው፣ "ጌታዬ ሆይ፤ በስንፍናችን የሠራነውን ኀጢአት እባክህ አትቍጠርብን። [12]እርሷንም በእናቱ ማሕፀን ሳለ ሞቶ ግማሽ አካሉ ከተበላ በኋላ የተወለደ ጭንጋፍ መስላ እንድትቀር አታድርግ።"

[13]ስለዚህም ሙሴ፣ "ስምሳክ (ኤሎሂም) ሆይ፤ እባክህ ፈውሳት" ብሎ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጮኸ።

[14]እግዚአብሔርም (ያህዌ) ለሙሴ፣ "አባቷ እፊቷ ላይ ቢተፋባት እስከ ሰባት ቀን በኀፍረት መቈየት አይገባትምን? አሁንም ከሰፈር ውጭ ሰባት ቀን እንድትገለል አድርግ፤ ከዚያ በኋላ ግን ልትመለስ ትችላለች" ሲል መለሰለት። [15]ስለዚህም ማርያም ከሰፈር ውጭ ሰባት ቀን ተገለለች፤ ከዚያ እስክትመለስም ሕዝቡ ጕዞውን አልቀጠለም ነበር።

[16]ከዚያ በኋላ ሕዝቡ ከሐጼሮት ተነሥተ፤ በፋራን ምድረ በዳም ሰፈረ።

12፥7 ዘጸ34፥5፤ኢያ 1፥1-2፤መዝ105፥26 ዕብ3፥2-5
12፥8 ዘፀ20፥41 24፥2፤መሳ14፥12፤ 1ነገ10፥1፤ኢዮ19፥26 1መዝ17፥15፤49፥4፤ 140፥13፤ምሳ1፥6፤ ኢሳ6፥1፤ዳን5፥12
12፥9 ዘፍ17፥22፤ ዘፀ4፥14
12፥10 ዘፀ4፥6፤ 40፥2፤ዘሌ13፥11፤ዘዳ 24፥9፤2ነገ5፥1፡27፤ 2ዜና16፥12፤21፥12-15፤26፥19
12፥11 2ሳሙ19፥ 19፤24፥10
12፥13 ዘፀ15፥26፤ መዝ6፥2፤147፥3፤ኢሳ 1፥6፤30፥26፤53፥5፤ ኤር17፥14፤ሆሴ6፥1
12፥14 ዘሌ13፥46፤ ዘዳ25፥9፤ኢዮ17፥6፤ 30፥9-10፤ኢሳ50፥6
12፥15 ዘሌ13፥4፤ 14፥8
12፥16 ዘፍ21፥21፤ ዘኍ11፥35፤10፥12፤ 15፥32
13፥2 ቍ16፤ዘዳ 1፥22፤ዘሌ14፥34፤ 24፥11፤ኢያ1፥3
13፥3 ዘኍ1፥16
13፥6 ቍ30፤ዘኍ 14፥6፡24፤34፥19፤ዘዳ 1፥36፤መሳ1፥12-15
13፥8 ዘኍ11፥28
13፥16 ቍ2፡8፤ ዘጸ32፥44
13፥17 ቍ2፤ኢያ 14፥7፤ዘፍ12፥9፤ዘዳ1፥ 7፤ኢያ9፥1፤መሳ1፥9

## ከነዓንን መሰለል

**13** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]"ለእስራኤላውያን የምሰጠውን የከነዓንን ምድር እንዲሰልሉ ጥቂት ሰዎች ላክ፤ ከእያንዳንዱም የአባቶች ነገድ አለቃ ይላክ።"

[3]ስለዚህ ሙሴ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ትእዛዝ ከፋራን ምድረ በዳ እነዚህን ላካቸው፤ ሁሉም የእስራኤላውያን አለቆች ነበሩ፤ [4]ስማቸውም እንደሚከተለው ነው፤

ከሮቤል ነገድ፣ የዘኩር ልጅ ሳሙኤል፤
[5]ከስምዖን ነገድ፣ የሱሬ ልጅ ሰፈጥ፤
[6]ከይሁዳ ነገድ፣ የዩፎኒ ልጅ ካሌብ፤
[7]ከይሳኮር ነገድ፣ የዮሴፍ ልጅ ይግአል፤
[8]ከኤፍሬም ነገድ፣ የነዌ ልጅ አውሴ፤
[9]ከብንያም ነገድ፣ የራፉ ልጅ ፈልጢ፤
[10]ከዛብሎን ነገድ፣ የሰዲ ልጅ ጉዲኤል፤
[11]ከምናሴ ነገድ ይህም የዮሴፍ ነገድ
ነው፤ የሱሲ ልጅ ጋዲ፤
[12]ከዳን ነገድ፣ የገማሊ ልጅ ዓሚኤል፤
[13]ከአሴር ነገድ፣ የሚካኤል ልጅ ሰቱር፤
[14]ከንፍታሌም ነገድ፣ የያቢ ልጅ ናቢ፤
[15]ከጋድ ነገድ፣ የማኪ ልጅ ጉዲኤል።

[16]እንግዲህ ምድሪቱን እንዲሰልሉ ሙሴ የላካቸው ሰዎች ስም ይህ ነው። ሙሴ ለነዌ ልጅ ለአውሴ፣ "ኢያሱ" የሚል ስም አወጣለት።

[17]ሙሴም ከነዓንን እንዲሰልሉ በላካቸው ጊዜ እንዲህ አላቸው፤ "ኔጌብን ዘልቃችሁ ወደ ተራራማው አገር ግቡ። [18]ምድሪቱ ምን እንደምትመስልና የሚኖሩባትም ሰዎች ብርቱዎች ወይም ደካሞች፣ ጥቂቶች ወይም ብዙዎች መሆናቸውን እዩ። [19]የሚኖሩባት

*10 በዕብራይስጡ ትርጕም ለምጽ ብቻ ሳይሆን፣ የተለያዩ የቆዳ በሽታዎችንም ያመለክታል።

ይኸውም ትክክለኛ ራእይ ሁሉ ከእግዚአብሔር ሲሆን፣ ሙሴን በተመለከተ ግን ያለበት ከፍተኛ የኀላፊነት ቦታና ታማኝነቱ ከእግዚአብሔር ጋር ያለውን ልዩ ግንኙነት ያጐላል።

12፥7 *ለአገልጋዬ፤* የዘፀ 14፥31 ማብ፤ ኢሳ 41፥8-9፤ 42፥1 ይመ። *ቤቴ፤* የእግዚአብሔር ወገን በሆነው የእስራኤል ቤተ ሰው ላይ ማለት ነው።

12፥8 *በግልጽ እንጂ በልዩ ዘይቤ፤* እግዚአብሔር ለአገልጋዮቹ የሚገለጠው ለሁሉም በአንድ ዐይነት መንገድ አይደለም። ይኸውም አንድ ነቢይ በወቅቱ ሙሉ በሙሉ ሊረዳው የማይችል ከእግዚአብሔር የሚሰጥ የትንቢት ቃል ይኖራል፤ ለነቢዩ እንቆቅልሽና ምስጢር ሊሆንበት ይችላል (ከ1ጴጥ 1፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ)። ለሙሴ ግን እግዚአብሔር ልዩ በሆነ ግልጸት ፊት ለፊት ሆኖ የመነጋገር ያህል አነጋግሮታል (ዘዳ 34፥10 በተጨማሪ ይመ)።

12፥10 *በለምጽ ተመታች፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። የወንድሟ የሙሴ ዋና ተቃዋሚ የሆነችው ማርያም አሁን ከእስራኤል ማኅበረ ሰብ እንድትገለል በሚያደርግ በለምጽ በሽታ ተመታች (5፥1-4 ይመ)።

12፥11 *ጌታዬ ሆይ!* ለተደረገው የድፍረት ኀጢአት በአሮን ላይ የሚታየው ንስሐ ፍጹም ከልብ መሆኑና ለእኅቱ (ለሙሴ እኅት) ያለውን አዘኔታ የሚገልጽ በመሆኑ ልብን የሚነካ ነው።

12፥14 *ሰባት ቀን በኀፍረት፤* በሕዝብ ፊት የሚያስወቅስ ተግባር (ዘዳ 25፥9 ይመ) ለተወሰነ ጊዜ በሕዝብ ፊት ኀፍረትን ያስከትላል። የሰው በድን የነካ ለሰባት ቀን ርኩስ ሆኖ እንዲቈይ ማድረግ የተለመደ ነበር (19፥11:14:16 ይመ)።

12፥16 *በፋራን ምድረ በዳ፤* የተስፋዪቱ ምድር ደቡባዊ ጫፍ ክልል ነው። በዚህ ጊዜ ሕዝቡ ድል አድርጎ ምድሪቱን ለመያዝ የቀረው ጥቂት ጊዜ ነበር።

13፥2 *የከነዓንን ምድር እንዲሰልሉ ጥቂት ሰዎች ላክ፤* በጥንቶቹ የቅርብ ምሥራቅ አገሮች መሰለል የተለመደ ተግባር ነበር (የኢያ 2፥1-24 ማብ ይመ)። ከዘዳ 1፥22-23 አንጻር እግዚአብሔር ይህን ትእዛዝ ለሙሴ የሰጠው፣ በሕዝቡ ጥያቄ ላይ ተመሥርቶ ይመስላል። ስለዚህ በዚህ ዘዴ ሰላዮችን የመላኩ ጕዳይ የእግዚአብሔርን ቸርነት የሚገልጽ ነበር።

*13፥4-15፤* እዚህ ላይ የተዘረዘሩት ስሞች በም 1-2፤ 7፤10 ላይ ከተጠቀሱት የተለዩ ናቸው። ቀደም ባሉት አራት ዝርዝሮች ውስጥ የተገለጹት የነገድ መሪዎች ሽምግል ያሉ ሰዎች ነበሩ ማለት ይቻላል። ለስለላ ተግባር የሚያስፈልጉ ሰዎች በዕድሜ ወጣቶች፣ በሰውነት አቋማቸውም ጠንከር ያሉ እንዲሆኑ ያስፈልግ ነበር፤ በጎደኞቻቸውም ዘንድ ከበሬታ ያላቸው ሰዎች ሊሆኑ ይገባል።

13፥16 *ሙሴ ለነዌ ልጅ ለአውሴ፣ "ኢያሱ" የሚል ስም አወጣለት፤* ኢያሱ ወደ ፊት ዕውቅ ሰው እንደሚሆን ለመጠቈም ያህል ለየት ብሎ የገባ ገለጻ ነው። ለመሰለል ከተላኩት ሰዎች የስም ዝርዝር ውስጥ ይህ ስም ትርጕም አዘል መሆኑን አንባቢው በንቃት እንዲያስተውል ተደርጎአል፤ ይህም ሰው ለወደፊት በሕይወቱ ትልቅ ቁም ነገር (ዐላማ) ይከናወንበታል። አውሴ ትርጕሙ "ድነት" ማለት ሲሆን፣ ኢያሱ ማለት ደግሞ "እግዚአብሔር ያድናል" ማለት ነው።

*13፥17-20፤* ሙሴ ለዐሥራ ሁለቱ ሰላዮች የሰጠው መመሪያ ብዙ ነገር ያካተተ ነበር። ይኸውም ስለ ምድሪቱና ስለምታስገኘው ምርት፣ ስለ ሕዝቦቿና ስለ ከተሞቿ፣ ስለሌላውም ስለ ለው የተሟላ ዘገባ ይዘው እንደሚመለሱ ይጠበቅባቸው ነበር።

ምድር ምን ዐይነት ናት? መልካም ወይስ መጥፎ? የሚኖሩባቸውስ ከተሞች ምን ይመስላሉ? በግንብ ያልታጠሩ ናቸው ወይስ የተመሸጉ? [20]ዐፈሩስ እንዴት ያለ ነው? ለም ወይስ ደረቅ? ደናም ወይስ ደን አልባ? በተቻለ መጠን ከምድሪቱ ፍሬ ይዛችሁ ኑ:: ወቅቱ የወይን ፍሬ መብሰል የጀመረበት ጊዜ ነበር::

[21]ስለዚህ ወጥተው ከጺን ምድረ በዳ አንሥቶ በሊቦ ሐማት በኩል እስከ ረአብ ድረስ ዘልቀው ምድሪቱን አጠኑ:: [22]በኔጌብ በኩል አልፈው አኪመን፣ ሴሲና ተላሚ የተባሉ የዔናቅ ዝርያዎች ወደሚኖሩበት ወደ ኬብሮን መጡ:: ኬብሮን የተመሠረተችው ጣኔዎስ በግብፅ ምድር ከመቈርቈሯ ሰባት ዓመት አስቀድሞ ነበር:: [23]ወደ ኤሽኮል[b] ሸለቆ በደረሱ ጊዜ የወይን ዘለላ ያንዠረገገ አንድ ቅርንጫፍ ቈረጡ፤ ይህንንም ከሮማንና ከበለስ ጋር በመሎጊያ አድርገው ለሁለት ተሸከሙት:: [24]እስራኤላውያን የወይን ዘለላ ስለ ቈረጡባትም ያች ስፍራ የኤሽኮል ሸለቆ ተባለች:: [25]ምድሪቱንም አሥሠው ከአርባ ቀን በኋላ ተመለሱ::

## ሰላዮቹ ያቀረቡት የአሠሣ ውጤት

[26]ሰዎቹም፣ ሙሴና አሮን መላውም የእስራኤላውያን ማኅበረ ሰብ ወዳሉበት በፋራን ምድረ በዳ ወደምትገኘው ወደ ቃዴስ ተመለሱ፤ ያዩትንም ለእነርሱና ለማኅበሩ ሁሉ አስረዱ፤ የምድሪቱንም ፍሬ አሳዩአቸው:: [27]ለሙሴም እንዲህ ብለው ነገሩት፤ "ወደ ላክኸን ምድር ዘልቀን ገባን፤ ማርና ወተት የምታፈስስ ናት፣ ፍሬዋም ይኸው:: [28]በዚያ የሚኖሩት ሰዎች ግን ኀያላን ሲሆኑ፣ ከተሞቹም የተመሸጉና ትላልቅ ናቸው፤ እንዲያውም የዔናቅን ዝርያዎች በዚያ አይተናል:: [29]አማሌቃውያን የሚኖሩት በኔጌብ፣ ኬጢያውያን ኢያቡሳውያንና አሞራውያን በኰረብታማው አገር፣ ከነዓናውያን የሚኖሩት ደግሞ በባሕሩ አቅራቢያና በዮርዳኖስ ዳርቻ ነው::"

[30]ከዚያም ካሌብ ሕዝቡን በሙሴ ፊት ጸጥ አሰኝቶ፣ "እንውጣ! ምድራቸውን እንውረስ፤ ማሸነፍም እንችላለን" አላቸው:: [31]ከእነርሱ ጋር የወጡት ሰዎች ግን፣ "ከእኛ ይልቅ ብርቱዎች ስለ ሆኑ፣ ልናሸንፋቸው አንችልም" አሉ:: [32]እንዲህም ስለ ሰለሏት ምድር በእስራኤላውያን መካከል እንዲህ የሚል መጥፎ ወሬ አሠራጩ፤ "ያየናት ምድር የሚኖሩባትን ሰዎች የምትበላ ናት፤ እዚያ ያየናቸው ሰዎች ሁሉ ግዙፎች ናቸው፤ [33]ኔፊሊምንም በዚያ አይተናል፤ የዔናቅ ዝርያዎች የመጡት ከኔፊሊም ነው:: ራሳችንን ስናየው እንደ አንበጣ ነበርን፤ በእነርሱ ዐይን የታየነውም በዚሁ መልክ ነበር::

## የሕዝቡ ማመፅ

**14** በዚያች ሌሊት ማኅበረ ሰቡ ሁሉ ድምፁን ከፍ አድርጎ ጮኸና አለቀሰ:: [2]እስራኤላውያን በሙሉ በሙሴና በአሮን ላይ አጕረመረሙ፤ ማኅበሩም ሁሉ እንዲህ አሉአቸው፤ "ምነው በግብፅ ወይም በዚህ ምድረ በዳ ሞተን ባረፍነው ኖሮ! [3]እግዚአብሔር (ያህዌ) ወደዚች ምድር የሚያመጣን ለምንድነው? በሰይፍ እንድንወድቅ ነውን?

13፥20 ዘዳ1፥25፤ ዘሌ25፥5
13፥21 ዘኍ20፥1፤ 34፥8፤27፥14፤33፥36፤ዘዳ32፥51፤ኢያ13፥5፤15፥1፤19፥28፤መሳ1፥31፤3፥3፤18፥28፤2ሳሙ10፥6፤1ነገ8፥65፤2ነገ14፥25፤1ዜና6፥75፤13፥5፤2ዜና7፥8፤ኤር52፥9፤ሕዝ47፥16፡20፤አሞ6፥14
13፥22 ቍ28፤ዘፍ13፥18፤23፥19፤ዘዳ2፥10፤9፥2፤ኢያ11፥21፤15፥13፡14፤መሳ1፥10፡20፤መዝ78፥12፡43፤ኢሳ19፥11፡13፤30፥4፤ሕዝ30፥14
13፥23 ዘፍ3፥7፤14፥13፤ዘፀ28፥33፤ዘኍ20፥5፤ዘዳ8፥8፤2ነገ18፥31፤ነህ13፥15
13፥25 ዘፍ7፥4፤ዘኍ14፥34
13፥26 ዘፍ14፥6፡7፤ዘኍ32፥8፤ዘዳ1፥25
13፥27 ዘፀ3፥8፤ዘዳ1፥25፤ኤር2፥7
13፥28 ቍ22፤ዘዳ1፥28፤9፥1፡2፤ኢያ14፥12
13፥29 ቍ17፤ዘፍ10፥15፡16፡18፤13፥10፤14፥7፤ዘፀ3፥8፤ዘኍ22፥1፤32፥5፤ዘዳ1፥1፤7፥1፤20፥17፤ኢያ1፥2፤መሳ3፥28፤1ነገ9፥20፤10፥29፤2ነገ7፥6፤መዝ42፥6
13፥30 ቍ6
13፥31 ዘዳ9፥1፤ኢያ14፥8
13፥32 ዘኍ14፥36፡37፤ዘዳ1፥28፤ሕዝ36፥13፡14፤አሞ2፥9
13፥33 ቍ28፤ዘፍ6፥4፤ዘዳ1፥28፤ኢያ11፥22፤14፥12፤መክ12፥5፤ኢሳ40፥22 14፥1 ዘፍ27፥38፤ዘፀ33፥4፤ዘኍ25፥6፤ዘዳ1፥45፤መሳ20፥23፡26፤2ሳሙ3፥32፤ኢዮ31፥29 14፥2 ዘፀ15፥24፤16፥3፤ዘኍ11፥1፤16፥13፡20፥4፤21፥5፤ዕብ3፥16 14፥3 ቍ31፤ዘፍ34፥29፤ዘፀ5፥21፤ዘዳ1፥39፤መዝ109፥11፤ኢሳ33፥4፤ሕዝ7፥21፤25፥7፤26፥5፤ሐሥ7፥39

[a]21 ወይም *በከተማዋ መግቢያ በኩል*
[b]23 ዘለላ ማለት ነው::

13፥21 ***ምድሪቱን አጠኑ፤*** የሰላዮቹ ጕዞ በምድሪቱ ደቡባዊ ዳርቻ ካለው ከጺን ምድረ በዳ ጀምሮ እስከ በሰሜናዊው ዳርቻ በሐማት አቅራቢያ እስካለው ሖር ተራራ ድረስ ይዘልቅ ነበር (34፥8 ይመ):: ይህ አራት መቶ ኪሎ ሜትር ርቀት ያለው ጕዞ አርባ ቀን (ቍ 25) የፈጀ ሲሆን፣ አርባ የተባለው ምናልባትም ዕጥፍ ቍጥር ሊሆን ይችላል::

13፥22 ***የዔናቅ ዝርያዎች፤*** ሦስት የታወቁ የዔናቅ ዘሮች በኬብሮን ይኖሩ እንደ ነበር ተገልጿል:: ዔናቃውያን በሰውነት አቋማቸው ግዙፎች ነበሩ፤ የቀመታቸውም ርዝማኔ በሰዎቹ ላይ ፍርሀት አሳድሮ ነበር (ቍ 32-33 ይመ):: ወደ ፊት በሚወሰደው የእምነት ርምጃ ካሌብ እነዚህን ሰዎች ከከተሞቻቸው አስወጥቶአቸዋል (ኢያ 15፥14፤ መሳ 1፥10):: ***ኬብሮን፤*** ሰላዮች ከነዓን ሲገቡ በመጀመሪያ ያገኙአት ከተማ ናት:: ከተማዋ በግብፅ ከነበረችው ከተማ ከጣኔዎስ ሰባት ዓመት ቀደም ብላ መቈርቈሯ በተጨማሪነት የተጠቀሰው ከአራት መቶ ዓመት በፊት ቀደም ብለው ከነበሩት ከአያቶቻቸው የአኗኗር ሁኔታ ጋር ተመሳሳይነት ስለሚታይባትና (ዘፍ 13፥14-18፤ 14፥12፤ 23፥2፤ 25፥9፤ 35፥27-29፤ 50፥13 ይመ) የከተማዋን መጠንና ቅጥር ከማድነቃቸው የተነሣ ሊሆን ይችላል:: በሕዝባቸው የዘር አመጣጥ ታሪክ ውስጥ ኬብሮን ትልቅ ከተማ አልነበረችም፤ እንዲያውም የከብት ጠባቂዎች መኖሪያና የንግድ ቦታ ነበረች::

13፥23 ***ኤሽኮል ሸለቆ፤*** ኤሽኮል ማለት፣ "ዘለላ" ማለት ነው:: ይህ ሸለቆ የሚገኘው በኬብሮን አጠገብ ነው፤ ሰላዮቹ ተልእኮአቸውን ፈጽመው ሲመለሱ የወይን ዘለላ ሳይቈርጡ አልቀሩም:: የወይኑም ዘለላ ትልቅነት እግዚአብሔር ሊሰጣቸው ያለውን ምድር መልካምነት አመልክቶአቸው ይሆናል::

*13፥26-29፤* የመጀመሪያው ክፍል የሰላዮቹ ዘገባ እውነት ሲሆን በዚያ የሚኖሩትን ኀይለኞች ሰዎች በመፍራታቸው የምድሪቱን መልካምነት እንዳያዩ ዐይናቸውን ሸፍኖአቸዋል::

13፥30 ***ካሌብ ሕዝቡን... ጸጥ አሰኝቶ፤*** በእግዚአብሔር ላይ ባላቸው እምነት የተደገፈ ዘገባ ያቀረቡት ካሌብና ኢያሱ ብቻ ነበሩ::

13፥32 ***ስለ ሰለሏት ምድር... መጥፎ ወሬ፤*** የዐሥሩ ሰላዮች አለማመን በሁለት አቅጣጫ ይታያል፤ (1) ባለፉት ጊዜያት እግዚአብሔር ለሕዝቡ ያሳየው ታማኝነት እነዚህን ዐሥር ሰዎች በእግዚአብሔር ታምነው እንዲቆሙ አላደረጋቸውም፤ (2) ለወደ ፊቱ ሕይወታቸውም በእግዚአብሔርና በሰጣቸው ተስፋ አልታመኑም (ከዘፍ 15፥18፤ 17፥8፤ ከዘፀ 33፥2 ጋር ያነጻጽሩ):: ተስፋ የተሰጣቸው ምድር መልካምና የእግዚአብሔር ቸር ስጦታ ነበረች:: እነዚህ እምነት የሌላቸው ሰላዮች ስለ ምድሪቱ መጥፎ ነገር ሲናገሩ፣ ስለ እግዚአብሔር ክፉኑት መናገራቸው ነበር (ከ10፥29 ጋር ያነጻጽሩ)::

*13፥33፤* የተናገሩት ነገር የተጋነነና የተዛባ ነበር:: የዔናቅ ሰዎች ኔፊሊም እንደ ሆኑ ተመልክቶአል (የዘፍ 6፥4 ማብ ይመ):: ኔፊሊም መሆናቸውን የገለጹት ሆን ብለው ፍርሀትን ለመፍጠር ያደረጉት ይመስላል:: እነዚህ በእግዚአብሔር የማይታመኑ ሰዎች በማጋነን መናገራቸው መጨረሻ ላይ ወደ ቂልነት መርቶአቸዋል፤ ይኸውም እኛ በእነርሱ ዘንድ "እንደ አንበጣ" የሆን ነበርን ብለዋል::

14፥1 ***ማኅበረ ሰቡ ሁሉ... አለቀሰ፤*** በእግዚአብሔር ያልታመኑ ሰላዮች የተናገሩት አስፈሪ ቃል ማኅበረ ሰቡ በሙሉ እንዲያለቅሱና በእግዚአብሔር ላይ ታላቅ ዐመፅ እንዲያካሄዱ አደረገ:: ከዚያ በፊት እግዚአብሔር ያደረገላቸውን ታምራት ሁሉ ረሱ፤ ምሕረቱንና ታላቅ ችሎታውን አቃለሉ:: በእግዚአብሔር ያልታመኑና ምስጋና ቢስ በመሆናቸው ሞትን መረጡ (ቍ 2)::

ሚስቶቻችንና ልጆቻችንም ይማረካሉ፤ ታዲያ ወደ ግብፅ መመለሱ አይሻለንም?" [4]እርስ በርሳቸውም፣ "አለቃ መርጠን ወደ ግብፅ እንመለስ" ተባባሉ::

[5]ከዚያም ሙሴና አሮን እዚያ በተሰበሰ ቡት በመላው እስራኤላውያን ማኅበር ፊት በግንባራቸው ተደፉ:: [6]ምድሪቱን ከሰለሏት መካከል የነበሩት የነዌ ልጅ ኢያሱና የዩ ፎኒ ልጅ ካሌብ ልብሳቸውን ቀደዱ፤ [7]ለመ ላው የእስራኤል ማኅበርም እንዲህ አሉ፤ 'ዞረን ያየናትና የሰለልናት ምድር እጅግ ሲበዛ መልካም ናት:: [8]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በእኛ ደስ ከተሰኘብን ማርና ወተት ወደምታፈ ሰው ወደዚያች ምድር መርቶ ያገባናል፤ ለእ ኛም ይሰጠናል:: [9]ብቻ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ላይ አታምፁ፤ እንደ እንጀራ እንጕርሳቸዋ ለንና የምድሪቱን ሰዎች አትፍሩአቸው:: ጥላ ቸው ተገፎአል፤ *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ከእኛ ጋር ነውና አትፍሯቸው::"

[10]መላው ማኅበር ግን በድንጋይ ሊወግሯ ቸው ተነጋገሩ፤ ከዚያም *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ክብር በመገናኛው ድንኳን ለእስራኤላ ውያን ሁሉ ተገለጠ:: [11]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "ይህ ሕዝብ እስከ መቼ ይንቀኛል? እነዚህን ሁሉ ታምራት በመካከሉ እያደረግሁ የማያምንብኝስ እስከ መቼ ነው? [12]በቸነፈር እመታዋለሁ፤ እደመ ስስዋለሁም፤ አንተን ግን ብርቱና ታላቅ ለሆነ ሕዝብ አደርግሃለሁ::"

[13]ሙሴ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዲህ አለው፤ "ነገሩን ግብፃውያን ቢሰሙትስ! ይህን ሕዝብ በኀይልህ ከመካከላቸው አውጥተኸዋልና፤ [14]የተ ደረገውንም በዚች ምድር ለሚኖሩት ሰዎች ይነግሯቸዋል:: *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሆይ፤ አንተ ከዚህ ሕዝብ ጋር መሆንህን፣ ደግ ሞም አንተ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሆይ፤ ፊት ለፊት እንደታየህና ደመናህ በላያቸው እንደ ሆነ፣ አንተም ቀን በደመና ዐምድ ሌሊ ትም በእሳት ዐምድ እፊት እፊታቸው እየ ሄድህ እንደ መራሃቸው ቀድሞውኑ ሰምተ

ዋል:: [15]ታዲያ ይህን ሁሉ ሕዝብ በአንድ ጊዜ ብትፈጀው ዝናህን የሰሙ ሕዝቦች፣ [16]'*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለዚህ ሕዝብ ይሰጠው ዘንድ በመሐላ ቃል ወደ ገባለት ምድር ሊ ያስገባው ባለመቻሉ በምድረ በዳ ፈጀው' ይሉሃል::

[17]"አሁንም እንዲህ ስትል በተናገርኸው መሠረት የጌታ ኀይል ይገለጥ፤ [18]'*እግዚአ ብሔር* (ያህዌ) ለቍጣ የዘገየ፣ ፍቅሩ የበዛ፣ ኀጢአትንና ዐመፃን ይቅር የሚል፣ በደለኛ ውን ግን ሳይቀጣ የማይተው፣ ስለ አባቶቻ ቸውም ኀጢአት ልጆችን እስከ ሦስትና አራት ትውልድ የሚቀጣ ነው::' [19]ከግብፅ ከወጡበት ጊዜ አንሥቶ እስካሁን ድረስ ይቅር እንዳልሃቸው ሁሉ እንደ ፍቅርህ ታላቅነት መጠን እባክህ አሁንም የዚህን ሕዝብ ኀጢ አት ይቅር በል::"

[20]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) እንዲህ ሲል መለ ሰለት፤ "በጠየቅኸው መሠረት ይቅር ብያቸ ዋለሁ፤ [21]ይሁን እንጂ ሕያው እንደመሆኔና *የእግዚአብሔርም* (ያህዌ) ክብር ምድርን ሁሉ የሞላ እንደ መሆኑ መጠን፣ [22]ክብሬን ደግ ሞም በግብፅና በምድረ በዳ ያደረግኋቸ ውን ታምራት አይተው ካልታዘዙኝና ዐሥር ጊዜ ከተፈታተኑኝ ሰዎች አንዳቸውም፣ [23]ለአ ባቶቻቸው እሰጣቸው ዘንድ በመሐላ ቃል የገባሁላቸውን ምድር አያዩዋትም:: የናቀኝ ማንኛውም ሰው ፈጽሞ አያያትም፤ [24]አገ ልጋዬ ካሌብ ግን የተለየ መንፈስ ስላለውና በፍጹም ልቡ የተከተለኝ በመሆኑ ሄዶባት ወደ ነበረችው ምድር አስገባዋለሁ፤ ዘሮቹም ይወርሷታል:: [25]አማሌቃውያንና ከነዓናው ያን በሸለቆው የሚኖሩ ስለ ሆነ በነገው ዕለት

14፥4 ነህ9፥17
14፥5 ዘሌ9፥24፤ 19፥2፤ዘኍ16፥4፤22፡ 45፤20፥6፤ኢሱ5፥14፤ 2ሳሙ14፥4፤1ዜና 21፥16፤ሕዝ1፥28
14፥6 ዘፍ37፥29፡ 34፤ዘኍ11፥28፤ መሳ11፥35፤ዕዝ9፥3፤ አስ4፥1፤2ሳሙ13፥31 ፤2ነገ19፥1፤ማር14፥63
14፥7 ዘኍ13፥27፤ ዘዳ1፥25
14፥8 ዘኍ13፥27፤ ዘዳ1፥21፥7፥8፥10፥15፤ መዝ18፥19፤22፥8፤37 ፥23፤41፥11፤56፥9፤ 147፥11፤ምሳ11፥20፤ ኢሳ62፥4፤ሚል2፥17
14፥9 ቍ24ዘፍ21፥ 22፤26፥24፤ዘዳ1፥21፡ 26፤30፤7፥18፤9፥7፡23 ፡24፤20፥1፤2ዜና13፥1 2፤32፥7፤መዝ118፥ 6፤ኤር15፥20፤41፥18 ፤42፥11፤46፥28፤ ሐጌ1፥13
14፥10 ዘፀ17፥4፤ 24፥16
14፥11 ዘፀ3፥20፤ 4፥17፤23፥21፤10፥1፤ ዘኍ15፥31፤16፥30፤ዘ ዳ1፥32፤1ሳሙ2፥17፤ ሕዝ31፥14፤ሚል1፥ 13፤መዝ78፥22፤ 106፥24፤ዮሐ3፥15
14፥12 ዘፀ5፥3፤ 30፥12፤32፥10፤ዘዳ9፥ 14፤29፥20፤32፥26፤ መዝ109፥13
14፥13 ዘፀ32፥11- 14፤መዝ106፥23
14፥14 ዘፀ13፥21፤ 15፥14፤33፥16፤ዘኍ 5፥3፤16፥3፤ዘዳ5፥4፤ 34፥10፤ኢሱ2፥9
14፥16 ዘፀ32፥12፤ ዘኍ11፥12፤ኢሱ7፥7
14፥18 ዘፀ20፥5፡6፤ 34፥6፤መዝ145፥8፤ ዮና4፥2፤ያዕ5፥11
14፥19 ዘፀ34፥9፤ 1ነገ8፥34፤መዝ78፥38 ፤85፥2፤103፥3፤106፥45
14፥20 ዘፀ34፥6፤ መዝ99፥8፤106፥23፤ ሚክ7፥18-20 14፥21 ቍ28፤ዘሌ9፥6፤ዘዳ32፥40፤መሳ8፥19፤ሩት3፥13፤ 1ሳሙ14፥39፤19፥6፤መዝ72፥19፤ኢሳ6፥3፤40፥5፤49፥18፤ ኤር4፥2፤ሕዝ5፥11፤ዕን2፥14፤ሶፎ2፥9 14፥22 ቍ11፤ዘፀ14፥11፤ 17፥7፤32፥1፤መዝ81፥7፤1ቆሮ10፥5 14፥23 ቍ11፡16፤ዘፀ33፥1፤ ዘኍ32፥11፤ዘዳ1፥34፤መዝ95፥11፤106፤26፤ዕብ3፥18 14፥24 ቍ 6-9፤ዘኍ13፥6፤26፥65፤32፥12፤ዘዳ1፥36፤ኢሱ14፥8፡14፤መዝ25፥13፤ 37፥9፡11 14፥25 ዘፍ10፥18፤14፥7፤ዘፀ23፥31፤ዘኍ21፥4፤14፥7፤ ዘዳ1፥40፤1ነገ9፥26

14፥3 *ልጆቻችን*፤ የእግዚአብሔርን ምሕረት በመዘንጋት ካሰቡት ማጕረምረም ሁሉ እጅግ የሚነቀፈው ስለ ልጆቻቸው የተናገሩት ነው:: በሕይወት የሚተርፉት ልጆቻቸው ብቻ ነበሩ (ቍ 31-33 ይመ)::

14፥9 *እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ነውና፤* እግዚአብሔር ከእ ነርሱ ጋር በሚሆንበት ጊዜ የእግዚአብሔርን ሕዝብ ሊቋቋምና በፊታቸውም ሊቆም የሚችል ቅጥር ወይም ምሽግ ወይም ግዙ ፍና ጠንካራ የሰውነት አቋም የለም፤ ባዕዳን አማልክትም እንኳ ቢሆኑ ሊቋቋሟቸው እንደማይችሉ የተረጋገጠ ነው::

14፥10 *የእግዚአብሔር ክብር... ተገለጠ፤* እግዚአብሔር የተገለጠው ድንገት በታላቅ ግርማና ቍጣ ስለ ነበር እጅግ ሳያ ስደነግጣቸው አልቀረም::

14፥11 *ይንቀኛል፤* የእስራኤል ሕዝብ በተለይ ካያቸውና ከተለማመደው ድንቅ ነገሮች አንጻር በእግዚአብሔር ኀይል አለ ማመኑ ለእግዚአብሔር ንቀት አሳይቶ እንደ ነበር ያመለክታል::

14፥12 *ሕዝብ አደርግሃለሁ፤* ታማኝ የሚሆነውን ሌላ ሕዝብ እንደሚያዘጋጅ፣ ሕዝቡ ከግብፅ ከወጡ በኋላ እግዚአብሔር ለሙሴ ሲናገር ሁለተኛ ጊዜው ነው (ዘፀ 32፥10 ይመ)::

14፥13 *ነገሩን ግብፃውያን ቢሰሙትስ!* ሙሴ ከራሱ ክብር ይልቅ ለእግዚአብሔር ስም የሚጠነቀቅ ራሱን ሙሉ በሙሉ ለእግዚአብሔር የሰጠ ሰው መሆኑን ያሳያል:: እግዚአብሔር ሕዝ ቡን ከግብፅ ባርነት ነጻ ማውጣቱን ከፍጻሜ ሊያደርስ እንዳልቻለ በመቍጠርና ኀይሉን በመናቅ የእግዚአብሔር ሕዝብ ጠላቶች በእግዚአብሔር ላይ ሊያላግጡ ይችላሉ::

*14፥17-19፤* እዚህ ላይ ሙሴ የእግዚአብሔርን ስም ከማስ ከበር ርእስ ጕዳይ ተመልሶ እግዚአብሔር ራሱ ስለ ጽኑ ፍቅሩና ሕዝ ቡን ለመገሠፅ ስለሚወስደው ርምጃ የተናገረውን አስማምቶና አቀነባብሮ በመጥቀስ ስለ እግዚአብሔር ባሕርይ ይገልጻል (ዘፀ 20፥6፤ 34፥6-7 ይመ)::

14፥22 *ዐሥር ጊዜ፤* ዝርዝሩ ቀጥሎ ባለው ሁኔታ ሊቀ ርብ ይችል ይሆናል (1) ዘፀ 14፥10-12፤ (2) ዘፀ 15፥22-24፤ (3) ዘፀ 16፥1-3፤ (4) ዘፀ 16፥19-20፤ (5) ዘፀ 16፥27-30፤ (6) ዘፀ 17፥1-4፤ (7) ዘፀ 32፥1-35፤ (8) ዘኍ 11፥1-3፤ (9) ዘኍ 11፥4-34፤ (10) ዘኍ 14፥3:: ነገር ግን "ዐሥር ጊዜ" ሲባል፣ "ብዙ ጊዜ" ለማለትም ይሆናል::

14፥24 *አገልጋዬ ካሌብ ግን የተለየ መንፈስ ስላለው፤* ካሌብ ብቻ ተለይቶ የተመረጠ ይመስላል፤ ምናልባት በቍ 7-9 የተጠቀሰውን የተናገረው ካሌብ ሊሆን ይችላል፤ ኢያሱም ሐሳ ቡን በመደገፍ የቀረበ ይመስላል:: ካሌብ ይበልጥ የተመሰከረለት ከአርባ አምስት ዓመት በኋላ ነው (የ13፥22 ማብ፣ ኢሱ 14፥10 ይመ)::

ተመልሳችሁ በቀይ ባሕር[*] መንገድ ወደ ምድረ በዳው ሂዱ::”

[26]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [27]“ይህ ክፉ ማኅበረ ሰብ በእኔ ላይ የሚያጕረመርመው እስከ መቼ ነው? የእነዚህን ነጭናጮች እስራኤላውያን ማጕረምረም ሰምቻለሁ:: [28]ስለዚህ እንዲህ በላቸው፤ ‘እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲህ ይላል፤ እኔ ሕያው ነኝ፤ ስትናገሩ የሰማኋችሁን እነዚያን ነገሮች አደርግባችኋለሁ፤ [29]በተደረገው ቈጠራ መሠረት፣ ሃያ ዓመት ወይም ከዚያ በላይ የሆናችሁና በእኔም ላይ ያጕረመረማችሁ ሁሉ በድናችሁ በዚህ ምድረ በዳ ይወድቃል:: [30]መኖሪያችሁ እንድትሆን በጽኑ ወደ ማልሁላችሁ ምድር ከዮፎኒ ልጅ ከካሌብና ከነዌ ልጅ ከኢያሱ በስተቀር ከእናንተ አንዳችሁም አትገቡባትም:: [31]ይማረካሉ ያላችኋቸውን ልጆቻችሁን ግን አገባቸዋለሁ፤ እናንተ የናቃችኋትን ምድር እነርሱ ይደሰቱባታል:: [32]እናንተ ግን፣ በድናችሁ በዚሁ ምድረ በዳ ወድቆ ይቀራል:: [33]ካለማመናችሁ የተነሣ ከእናንተ የመጨረሻው በድን እዚሁ ምድረ በዳ እስኪወድቅ ድረስ፣ ልጆቻችሁ መከራ እየበሉ አርባ ዓመት እረኞች ይሆናሉ:: [34]ምድሪቱን ለመሰለል በቈያችሁበት አርባ ቀን ልክ እያንዳንዱ ዓመት እንደ አንድ ዕለት ተቈጥሮ ስለ ኀጢአታችሁ አርባ ዓመት መከራ ትቀበላላችሁ፤ ምን ያህል በእናንተ ላይ እንደ ተነሣሁም ታውቃላችሁ:: [35]እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) ይህን ተናግሬአለሁ፤ ደግሞም አንድ ሆኖ በተነሣብኝ በዚህ ክፉ ማኅበረ ሰብ ሁሉ ላይ እነዚህን ነገሮች አደርጋለሁ፤ መጨረሻቸው በዚሁ ምድረ በዳ ይሆናል፤ እዚሁም ይሞታሉ::’ ”

[36]ከዚህ በኋላ ምድሪቱን እንዲሰልሉ ሙሴ ልኳቸው የነበሩትና ከዚያ ተመልሰው ስለ ምድሪቱ ክፉ ወሬ በማሠራጨት ማኅበረ ሰቡ በሙሉ እንዲያጕረመርሙበት ያደረጉ፣ [37]ስለ ምድሪቱም ክፉ ወሬ በማሠራጨት ተጠያቂ የሆኑት እነዚሁ ሰዎች ተቀሥፈው በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ሞቱ:: [38]ምድሪቱን እንዲሰልሉ ከተላኩት ሰዎች በሕይወት የተረፉት የነዌ ልጅ ኢያሱና የዮፎኒ ልጅ ካሌብ ብቻ ነበሩ::

[39]ሙሴም ይህን ለእስራኤላውያን ሁሉ በነገራቸው ጊዜ ክፉኛ አዘኑ:: [40]በማግሥቱም ጠዋት ማለዳው ወደ ተራራማው አገር ወጡ፤ እንዲህም አሉ፣ “ኀጢአት ሠርተናልና እግዚአብሔር (ያህዌ) ተስፋ ወደ ሰጠን ስፍራ እንወጣለን”::

[41]ሙሴ ግን እንዲህ አለ፤ “የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ትእዛዝ ለምን ትጥሳላችሁ? ይህም አይሳካላችሁም! [42]እግዚአብሔር (ያህዌ) ከእናንተ ጋር ስላይደለ አትውጡ፤ በጠላቶቻችሁ ድል ትመታላችሁ፤ [43]አማሌቃውያንና ከነዓናውያን በዚያ ያጋጥሟችኋልና:: እግዚአብሔርን (ያህዌ) ስለተዋችሁትና እርሱም ከእናንተ ጋር ስለማይሆን በሰይፍ ትወድቃላችሁ::”

[44]ሙሴም ሆነ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ታቦት ከሰፈር ሳይነሡ በስሜት ተገፋፍተው ብቻ ወደ ተራራማው አገር ወጡ:: [45]በዚህ ጊዜ በተራራማው አገር የሚኖሩት አማሌቃውያንና ከነዓናውያን ወርደው ወጉአቸው፤ እስከ ሔርማ ድረስም አሳደዱአቸው::

## ተጨማሪ ቍርባን

**15** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]“እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ ‘እንድትኖሩበት ወደምሰጣችሁ ምድር ከገባችሁ በኋላ፣ [3]ስእለታችሁን ለመፈፀም ወይም የበጎ ፈቃድ ስጦታ ለማድረግ ወይም በተወሰኑ በዓሎቻችሁ ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ መሥዋዕት ከላም ወይም ከበግ መንጋ በእሳት ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ስታቀርቡ

[*]25 በዕብራይስጥ ትርጕሙ ያም ሱፍ የሚል ሲሆን የሸምበቆ ባሕር ማለት ነው::

14፥27 ዘፀ16፥12፤ ዘዳ1፥34:35
14፥28 ቍ21፤ዘኍ 33፥56
14፥29 ቍ23:30: 32፤ዘፀ30፥12፤ዘኍ1፥ 45፤26፥65፤32፥13፤ 1ቆሮ10፥5፤ዕብ3፥ 17፤ይሁ1፥5
14፥30 ቍ29፤ዘፀ 6፥8፤ዘኍ11፥28፤13፥ 6፤ዘዳ32፥40፤ነህ9፥15 ፤መዝ106፥26፤ሕዝ 20፥5፤36፥7
14፥31 ዘሌ26፥43
14፥32 ቍ29:35
14፥33 ቍ34፤ዘፀ 16፥35፤ሐሥ13፥18፤ ዕብ3፥9
14፥34 ቍ33፤ ዘኍ13፥25
14፥35 ቍ32 ዘኍ23፥19
14፥36 ቍ2፤ዘኍ 13፥4-16:32
14፥37 ዘኍ13፥32፤ 16፥49፤25፥9፤26፥1፤ 31፥16፤1ቆሮ10፥10፤ ዕብ3፥17፤ዘዳ4፥3
14፥38 ቍ24:30፤ 32ዘኍ13፥4-16፤ ኢሱ14፥6
14፥39 ቍ28-35፤ ዘፀ33፥4
14፥40 ቍ45፤ዘኍ 13፥17፤ዘፀ9፥27
14፥41 2ዜና24፥20
14፥42 ዘዳ1፥42
14፥43 ቍ45፤ዘፍ 39፥23፤ዘኍ13፥29፤ መሳ1፥19፤3፥13፤ዘዳ 31፥8፤ኢሱ6፥27፤መሳ 1፥19፤6፥16፤1ሳሙ3፥ 19፤18፥14፤2ዜና1፥1
14፥44 ዘኍ31፥6፤ ዘዳ1፥43
14፥45 ቍ40:43፤ ዘኍ21፥3፤ዘዳ1፥44፤ ኢሱ12፥14፤15፥30፤ 19፥4፤መሳ1፥17፤1ሳ ሙ30፥30፤1ዜና4፥30
15፥2 ዘሌ23፥10
15፥3 ቍ24፤ዘሌ 1፥2:3፤9፤7፥16፤

14፥28 *ስትናገሩ የሰማኋችሁን እነዚያን ነገሮች አደርግባችኋለሁ፤* የእስራኤል ሕዝቦች ቅጣታቸውን በራሳቸው ላይ አመጡ:: በሰይፍ ለመሞት ከነዓን ከሚገቡ በምድረ በዳ ቢሞቱ እንደሚሻላቸው ተናግረው ነበር (ቍ 2):: በሕዝብ ቈጠራው ወቅት ዕድሜያቸው ሃያና ከዚያም በላይ የሆኑት ሁሉ በምድረ በዳ እንደሚሞቱ ተነገራቸው (ቍ 29)፤ ይህም ኢያሱና ካሌብ ብቻ ሲቀሩ ነው (ቍ 30):: እግዚአብሔር፣ ልጆቻችን በምድረ በዳ እንዲሞቱብን አድርጎአል ያሉአቸው (ቍ 3) የሚተርፉት ልጆቻቸው ብቻ ሆኑ (ቍ 31)::

*14፥34፤* ሰላዮቹ አርባ ቀን መጓዛቸው ሕዝቡ በበረሓ ስለ መንከራተቱ አጓዙ የሚያመለክተው ምሳሌ ነበረው፤ አንድ ቀን እንደ አንድ ዓመት የሚቈጠር ሲሆን፣ የተዛባ ፍርድ አሰጣጣቸውን አርባ ዓመት ሙሉ ያሰላስላሉ፤ ደግሞም ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ የሆኑት ሁሉ በአርባ ዓመት ጊዜ ውስጥ ሞተው ያልቃሉ፤ ስለዚህ ወደ ከነዓን ምድር የሚገባው አዲሱ ትውልድ ብቻ ይሆናል:: እስራኤል ምድሩን ድል አድርጋ ትወርስ ዘንድ እግዚአብሔር ለሰጣት ተልእኮ አለመታዘዟ እግዚአብሔርን ያስቈጣ እስራኤልም በምድረ በዳ እንድትቀር ያደረገ ከፍተኛ ዐመፅ ነው::

14፥37 ***ክፉ ወሬ በማሠራጨት፣ ተጠያቂ የሆኑት እነዚሁ ሰዎች ተቀሥፈው ... ሞቱ፤*** በዐሥሩ ክፉዎቹ ሰላዮች ላይ የተሰጠው የቅጣት ፍርድ ፈጣን ነበር፤ እነርሱ በክፉ ወሬ የበከሏቸው ሰዎች በምድረ በዳ ዕድሜያቸው የፈቀደውን ያህል መኖር ቀጠሉ::

14፥40 ***እንወጣለን፤*** ሕዝቦች አንወጣም ወዳሉት ምድር ሊወጡ ወሰኑ፤ ነገር ግን ጊዜው አልፎባቸዋል፤ ከንቱ ልፋትም ነበር:: እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር ያለመሆኑ ብቻ ሳይሆን ይዋጋቸውም ነበር (ቍ 41):: በመቀጠልም የሚገጥማቸው ሽንፈት (ቍ 45) ዐመፀኞቹ ሰዎች በገዛ ራሳቸው ላይ ያመጡት ሌላው ቅጣት ነበር::

*15፥1-41፤* ይህ ምዕራፍ በሦስት ክፍል ተከፍሎአል፤ እያንዳንዱም ክፍል፣ “እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ አለው” (ቍ 1፡ 17:37) በሚል ሐረግ ይጀምራል:: ሕዝቦች ግልጽ የሆነውን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ባለመታዘዛቸው ምክንያት ለማንነቱም ክብር ስላልሰጡ በከፋ ቅጣት ሥር ወድቀው ነበር::

15፥2 ***ወደምሰጣችሁ ምድር ከገባችሁ በኋላ፤*** የም 14 አሳዛኝ ፍጻሜ ከዚህ ሐረግ ጋር ጐን ለጐን መቀመጡ ዐይን የሚስብ አቀራረብ ነው:: የሕዝቡ ኀጢአት ብዙ ዐይነት በመሆኑ ፍርድ ይጠብቀዋል:: እግዚአብሔር ጥንት ለአብርሃም የገባውን ቃል ማሰቡ (ዘፍ 12፥7) ደግሞም አሁን ሕዝቡ ወደ ተስፋዪቱ ምድር እንደሚገባ ማረጋገጡ፣ ጸጋውንና ምሕረቱን አጕልቶ ያሳያል::

*15፥3-12፤* የእህልና የወይን ጠጅ ቍርባን ከሚቃጠል መሥዋዕት ጋር ይቀርብ ነበር፤ እህሉም በዘይት ይለወሳል:: ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚቀርበው እንስሳ መጠን ከፍ ሲል እንዲሁም የእህሉ ቍርባን መጠን ይጨምር ነበር (ቍ 6-12):: ከሚቃጠል መሥ

[4]መሥዋዕቱን ይዞ የሚመጣው ሰው በኢን[a] አንድ አራተኛ ዘይት የተለወሰ የኢፍ[b] አንድ ዐሥረኛ የላመ ዱቄት የእህል ቍርባን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ያቀርባል። [5]ለሚቃጠል ወይም ለዕርድ መሥዋዕት ከሚቀርብ ከእያንዳንዱ የበግ ጠቦት ጋር የኢን አንድ አራተኛ የወይን ጠጅ የመጠጥ ቍርባን አብራችሁ አዘጋጁ።

[6]“ ‘ከአውራ በግ ጋር በኢን[c] ሢሶ ዘይት የተለወሰ የኢፍ[d] ሁለት ዐሥረኛ ልም ዱቄት የእህል ቍርባን አዘጋጁ፤ [7]እንዲሁም ለመጠጥ ቍርባን የሚሆን የኢን አንድ ሦስተኛ የወይን ጠጅ አዘጋጁ፤ ይህንም እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ ሽታ ያለው አድርጋችሁ አቅርቡ።

[8]“ ‘አንዱን ወይፈን ለተለየ ስለት ወይም ለኅብረት የሚቀርብ የሚቃጠል መሥዋዕት[e] ወይም የዕርድ መሥዋዕት አድርጋችሁ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) በምታዘጋጁበት ጊዜ፣ [9]ከወይፈኑ ጋር በግማሽ ኢን[f] ዘይት የተለወሰ የኢፍ[g] ሦስት ዐሥረኛ የላመ ዱቄት አብራችሁ አምጡ። [10]እንዲሁም ለመጠጥ ቍርባን የሚሆን ግማሽ ኢን የወይን ጠጅ አቅርቡ፤ ይህም በእሳት የሚቀርብና ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ መሥዋዕት ይሆናል። [11]እያንዳንዱ ወይፈን ወይም አውራ በግ፣ እያንዳንዱ የበግም ሆነ የፍየል ጠቦት በዚህ ሁኔታ ይዘጋጅ። [12]ባዘጋጃችሁት ቍጥር ልክ ይህን ለእያንዳንዱ አድርጉ።

[13]ማናቸውም የአገር ተወላጅ የሆነ በእሳት የሚቀርብ ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ መሥዋዕት በሚያቀርብበት ጊዜ እነዚህን ነገሮች በዚሁ ሁኔታ ያድርግ። [14]ለሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ መጻተኛ ወይም በመካከላችሁ የሚኖር ማናቸውም ሰው በእሳት የሚቀርብ ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ መሥዋዕት በሚያቀርብበት ጊዜ ልክ እናንተ እንደምታደርጉት ያድርግ። [15]ማኅበረ ሰቡ ለእናንተም ሆነ በመካከላችሁ ለሚኖር መጻተኛ አንድ ዐይነት ደንብ ይኖረዋል፤ ይህም በሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ የማይሻር ሥርዐት ነው። እናንተም ሆናችሁ መጻተኞቹ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት እኩል ትታያላችሁ፤ [16]ለእናንተም ሆነ በመካከላችሁ ለሚኖር መጻተኛ ይኸው ሕግና ሥርዐት እኩል ተፈጻሚነት ይኖረዋል።’ ”

[17]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤

23፥1-44፤ዘኍ 28፥13፤ዕዝ1፥4
15፥4 ዘፀ16፥36፤ ዘሌ6፥14
15፥5 ዘፍ35፥14፤ ዘሌ3፥7፤10፥9
15፥6 ዘሌ5፥15፤ 23፥13፤ዘኍ28፥12፤ 29፥14፤ሕዝ46፥14
15፥7 ቍ5፤ዘሌ 1፥9፤23፥13፤ዘኍ 28፥14፤29፥18
15፥8 ዘፀ12፥5፤ ዘሌ1፥5፤3፥6፤22፥18
15፥9 ዘሌ2፥1፤ 14፥10
15፥10 ዘሌ1፥9፤ 23፥13፤ዘኍ28፥14
15፥12 ዕዝ7፥17
15፥13 ዘሌ1፥9፤ 16፥29
15፥14 ቍ25፤ዘፀ 12፥19፤43፤22፥21፤ ዘሌ3፥17፤22፥18፤ ዘኍ10፥8
15፥15 ቍ14:21
15፥16 ዘፀ12፥49፤ ዘሌ22፥18፤ዘኍ9፥14
15፥18 ዘሌ23፥10
15፥19 ዘኍ18፥8፤ ኢሱ5፥11፡12
15፥20 ዘፍ50፥10፤ ዘሌ2፥14፤23፥14፤ ዘኍ18፥27
15፥21 ዘሌ23፥14 ፤ሕዝ44፥30፤ሮሜ 11፥16
15፥22 ዘሌ4፥2
15፥23 ቍ21
15፥24 ቍ3፡25፡ 26፤ዘሌ5፥15፤4፥14፤ 2፥1፤23፥13፤4፥3፤ ዘኍ6፥15
15፥25 ቍ14:22: 24፤ዘሌ4፥3፥20፤ ሮሜ3፥25
15፥26 ቍ24
15፥27 ዘሌ4፥3: 27፤ዘኍ6፥14
15፥28 ዘሌ4፥20፤ ዘኍ8፥12፤28፥22

[18]“እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ ‘እኔ ወደምወስዳችሁ ምድር ገብ ታችሁ፣ [19]የምድሪቱን በረከት ስትመገቡ ከዚሁ ላይ አንሥታችሁ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ቍርባን አቅርቡ። [20]ይህንም ከመጀመሪያው ዱቄት ላይ ኅብስት ጋግራችሁ ከዐውድማ እንደ ተገኘ ቍርባን አድርጋችሁ አምጡ። [21]በሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ ከመጀመሪያው ዱቄት ላይ አንሥታችሁ ይህን ቍርባን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ትሰጣላችሁ።

## ባለማወቅ ስለሚደረግ ኀጢአት የሚቀርብ መሥዋዕት

[22]“ ‘እንግዲህ ካለማወቅ የተነሣ እግዚአብሔር (ለያህዌ) ለሙሴ ከሰጣቸው ትእዛዛት አንዱን ሳትፈጽሙ ብትቀሩ፣ ይህም ማለት [23]እግዚአብሔር (ያህዌ) ትእዛዛቱን ከሰጠበት ዕለት ጀምሮ በተከታታይ ትውልዶች በሙሴ አማካይነት ያዘዛችሁን እነዚህን ትእዛዛት ሁሉ ባታደርጉ፣ [24]ይህም የተፈጸመው ሆን ተብሎ ሳይሆንና ማኅበረ ሰቡም ሳያውቀው ከሆነ፣ ማኅበረ ሰቡ በሙሉ ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ አድርጎ አንድ ወይፈን በእሳት ለሚቃጠል መሥዋዕት ያቅርብ፤ ከዚሁም ጋር ሥርዐቱ የሚጠይቀውን የእህል ቍርባንና የመጠጥ ቍርባን ደግሞም ለኀጢአት መሥዋዕት ተባዕት ፍየል ያቅርብ። [25]ካህኑም ለመላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ያስተሰርያል፤ እነርሱም ይቅር ይባላሉ፤ ምክንያቱም ባለማወቅ የተፈጸመ ስለ ሆነና ስለ ስሕተታቸውም በእሳት የሚቃጠል መሥዋዕትና የኀጢአት መሥዋዕት ለእግዚአብሔር (ለያህዌ) ስላቀረቡ ነው። [26]ባለማወቅ የተደረገውን ስሕተት ሁሉም የፈጸሙት ስለ ሆነ፣ መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብና በመካከላቸው የሚኖር መጻተኛ ሁሉ ይቅር ይባላል።

[27]“ ‘ነገር ግን አንድ ሰው ካለማወቅ የተነሣ በግሉ ኀጢአት ቢሠራ ግን ለኀጢአት መሥዋዕት የአንድ ዓመት እንስት ፍየል ያምጣ። [28]ከዚያም ካህኑ፣ ባለማወቅ ኀጢአት ሠርቶ ለተሣሣተው ሰው በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ያስተሰርይለታል፤ ስርየት

[a]4 ሁለት ሊትር ያህል ነው። [b]4 አንድ ሊትር ያህል ነው።
[c]6 አራት ተኩል ሊትር ያህል ነው።
[d]6 አንድ ሊትር ያህል ነው።
[e]8 በተለምዶ የድነት መሥዋዕት ይባላል።
[f]9 ስድስት ተኩል ሊትር ያህል ነው።
[g]9 ሁለት ሊትር ያህል ነው።

ዋዕትና ከኅብረት መሥዋዕት ሁሉ ጋር የወይን ጠጅ ቍርባን አብሮ መቅረብ እንዳለበት ለመጀመሪያ ጊዜ የተመለከተው በዚህ ክፍል ላይ ነው።

15፥14 *መጻተኛ፤* የፋሲካ በዓል በሚከበርበት ጊዜ እንደሚደረገው ሁሉ (የ9፥14 ማብ ይመ) መጻተኛ የሆነ ሰው በትውልዱ እስራኤላዊ ከሆነ ሰው ጋር አንድ ዐይነት ደንብና ሥርዐት ይከተል ነበር። የራሳቸውን እምነት ጥለው የእስራኤልን እምነት ለሚቀበሉ ሰዎች የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ሁል ጊዜ ክፍት ነበር። በእርግጥም የእስራኤል መሠረተ እምነት በምድር ላይ የሚኖረውን ሰው ሁሉ የሚያቅፍ ነው (ዘፍ 12፥3)።

15፥20 *ከመጀመሪያው ዱቄት ላይ ኅብስት ጋግራችሁ... አምጡ፤* ይህ ሕግ እስራኤላውያን ወደ ምድሪቱ በሚገቡበት ጊዜ የሚሆነውን በደስታና በጕጕት እንዲጠብቁት ያደርጋል። መጀመሪያ ከሚወቃው እህል ኅብስት ተሠርቶ ለእግዚአብሔር መቅረብ ነበረበት። ከዕርሻ የመጀመሪያው ፍሬ የማቅረቡ ሐሳብ፣ በረከት ሁሉ ከእርሱ እንደሆነና ምርት ሁሉ የእርሱ እንደ ሆነ የሚያመለክት ምሳሌ ነው።

15፥22 *ካለማወቅ የተነሣ... ሳትፈጽሙ ብትቀሩ፤* ኀጢአት ባለማወቅ ሊሠራ ወይም ሊፈጸም ይቻላል፤ ሆኖም የመንጻት ሥርዐት መደረግ አለበት (የዘሌ 4፥2 ማብ ይመ)። ባለማወቅ የሚደረግ እንደዚህ ያለው ኀጢአት በሕዝቡ ሁሉ (ቍ 22-26) ወይም በአንድ ግለሰብ ( ቍ 22-29) ሊፈጸም ይችላል።

በሚደረግለትም ጊዜ ሰውየው ይቅር ይባላል። [29]*ያገር ተወላጅ እስራኤላዊ ይሁን ወይም መጻተኛ ባለማወቅ ኀጢአት ከሠራ በማና ቸውም ሰው ላይ ሕጉ እኩል ተፈጻሚነት ይኖረዋል።*

[30]" '*ያገር ተወላጅም ይሁን መጻተኛ ሆን ብሎ ኀጢአት የሚሠራ ማንኛውም ሰው ግን እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ስለሚያቃልል ያ ሰው ከወገኖቹ ተለይቶ ይጥፋ። [31]*የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ቃል ስለ ናቀ፣ ትእዛዛቱንም ስለ ጣሰ ያ ሰው በእርግጥ ተለይቶ መጥፋት አለ በት፤ ጥፋቱ የራሱ ነው።' "

## ሰንበትን የሻረው በሞት ተቀጣ

[32]እስራኤላውያን በምድረ በዳ በነበሩበት ጊዜ አንድ ሰው በሰንበት ቀን ዕንጨት ሲለቅም ተገኘ። [33]ዕንጨት ሲለቅም ያገኙ ትም ሰዎች ሰውየውን ወደ ሙሴ፣ ወደ አሮንና ወደ መላው የእስራኤል ማኅበር አመጡት፤ [34]በሰውየው ላይ ምን መደረግ እንዳለበት ግልጽ የሆነ ነገር ባለመኖሩ በጥ በቃ ሥር እንዲቈይ አደረጉት። [35]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን፣ "ሰውየው ይሙት፤ መላውም ማኅበር ከሰፈር ውጭ በድንጋይ ይውገረው" አለው፤ [36]ስለዚህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ማኅበሩ ሰውየውን ከሰፈር አውጥቶ እስኪሞት ድረስ በድንጋይ ወገረው።

## ስለ ልብስ ዘርፍ የተሰጠ መመሪያ

[37]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [38]"እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ 'በሚቀጥሉት ትውልዶች ሁሉ በየልብሳችሁ ጫፍ ላይ ዘርፍ አድርጉ፤ እያ ንዳንዱም ዘርፍ ሰማያዊ ጥለት ይኑረው። [39]ልባችሁ የተመኘውን፣ ዐይናችሁ ያየውን ሁሉ ተከትላችሁ እንዳታመነዝሩ እነዚህን ዘርፎች በማየት *የእግዚአብሔርን* (የያህዌ) ትእዛዛት በማስታወስ እንድትታዘዙ ማስታ ወሻ ይሆኑአችኋል። [40]ስለዚህ ትእዛዛቴን ሁሉ ለመፈጸም ታስባላችሁ፤ ለአምላካችሁም (ኤሎሂም) የተቀደሳችሁ ትሆናላችሁ። [41]አምላካ ችሁ (ኤሎሂም) እሆን ዘንድ ከግብፅ ምድር ያወ ጣኋችሁ እኔ አምላካችሁ *እግዚአብሔር* (ኤሎሂም ያህዌ) ነኝ። እኔ *እግዚአብሔር* አምላካችሁ (ያህዌ ኤሎሂም) ነኝ።'"

## ቆሬ፣ ዳታንና አቤሮን

**16** የሌዊ ልጅ፣ የቀዓት ልጅ፣ የይስዓር ልጅ የሆነው ቆሬ፣ ከሮቤልም ነገድ የኤልያብ ልጆች ዳታንና አቤሮን እንዲ ሁም የፍሌት ልጅ ኦን በክፉት ተነሣሥ ተው፣ [2]ሙሴን ተቃወሙት። ከእነዚህም ጋር ታዋቂ የማኅበረ ሰቡ መሪዎች የሆኑና በጉባኤ አባልነት የተመረጡ ሁለት መቶ አምሳ እስራኤላውያን አብረው ነበሩ። [3]እነ ዚህም ሙሴንና አሮንን ለመቃወም ግን ባር ፈጥረው በመምጣት፣ "ምነው ከልክ አላለፋችሁም! የማኅበረ ሰቡ አባላት ሁሉ እያንዳንዳቸው የተቀደሱ ናቸው፤ *እግዚአ ብሔርም* (ያህዌ) ከእነርሱ ጋር ነው፤ ታዲያ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ማኅበር ላይ የምትታ በዩት ለምንድነው?" አሉአቸው።

[4]ሙሴም ይህን ሲሰማ በግንባሩ መሬት ላይ ተደፋ፤ [5]ቆሬንና ተከታዮቹን በሙሉ እንዲህ አላቸው፤ "የእርሱ የሆነውና የተቀ ደሰው ማን መሆኑን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነገ ጠዋት ይለያል፤ ወደ ራሱም ያመጣዋል፤ የሚመርጠውን ሰው ወደ ራሱ እንዲቀርብ ያደርገዋል። [6]ቆሬ፣ አንተና ተከታዮችህ ሁሉ እንዲህ አድርጉ፤ ጥናዎችን ውሰዱ፤ [7]በማ ግስቱም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት እሳትና ዕጣን ጨምሩባቸው፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚመርጠውም ያ ሰው ቅዱስ ይሆናል፤ እናንተ የሌዊ ልጆች፤ ከልክ ያለፋችሁትስ እናንተ ናችሁ!"

[8]ደግሞም ሙሴ ቆሬን እንዲህ አለው፤ "እናንተ ሌዋውያን አድምጡ! [9]የእስራኤል አምላክ (ኤሎሂም) እናንተን ከቀሩት እስራኤላ

15፥29 ዘፀ12፥49
15፥30 ቍ14፤ዘፍ 17፥14፤ዘኍ14፥40-44፤ዘዳ1፥43፤17፥13፤ ኢዮ31፥22፤መዝ19፥13፤2ነገ19፥6፡20፤ኢሳ 37፥6፡23፤ሕዝ20፥27
15፥31 ዘሌ5፥1፤ዘኍ 14፥11፤1ሳሙ15፥23፡ 26፤2ሳሙ11፥27፤ 12፥9፤መዝ119፥126፤ ምሳ13፥13፤ሕዝ18፥20
15፥32 ዘፀ31፥14፡ 15፤35፥2፡3፤ዘኍ12፥16
15፥34 ዘኍ9፥8
15፥35 ዘፀ31፥14፡ 15፤ዘሌ20፥2፤ሉቃ 4፥29፤ሐሥ7፥58
15፥36 ዘፀ31፥14፤ ዘሌ20፥2፤ኤር17፥21
15፥38 ዘሌ3፥17፤ ዘኍ10፥8፤ዘዳ22፥12፤ ማቴ23፥5
15፥39 ዘሌ17፥7፤ ዘዳ4፥23፤6፥12፤መሳ 2፥17፤መዝ73፥27፤78 ፥37፤106፥39ኤር3፥2 17፥24፤ሕዝ20፥16፤ ሆሴ4፥12
15፥40 ዘፍ26፥5፤ ዘሌ11፥44፤ዘዳ11፥13 ፤መዝ103፥18፤119፥ 56፤ሮሜ12፥1፤ቈላ 1፥22፤1ጴጥ1፥15
15፥41 ዘፍ17፥7፤ ዘፀ20፥2
16፥1 ቍ24፤ዘፀ 6፥24፤ዘኍ26፥8፤ዘዳ 11፥6፤መዝ106፥17፤ ይሁ1፥11
16፥2 ዘኍ1፥16፤ 26፥9፤27፥3
16፥3 ቍ7፤ዘፀ 19፥6፤ዘኍ12፥2፤ 14፥14፤መዝ106፥16
16፥4 ዘኍ14፥5
16፥5 ዘሌ10፥3፤ ዘኍ17፥5፤መዝ65፥4፤ 105፥26፤ኤር30፥21፤ 50፥44፤2ጢሞ2፥19
16፥6 ቍ7፡16፤ ዘሌ10፥1፤ራእ8፥3
16፥7 ቍ5፡6፤ ዘሌ10፥1፤ዘፀ30፥9

15፥30 *ሆን ብሎ፤* ቀጥተኛ ትርጕሙ፣ "በትዕቢት ወይም በዕብሪት" ማለት ነው። ሳያውቅ ኀጢአትን የሚሠራ ከእግዚ አብሔር ምሕረት ያገኛል፤ ነገር ግን የእግዚአብሔርን ቃል የሚ ያቃልል ስሙንም የሚንቅና ለመሳደብ በትዕቢት የሚነሣሣ ሰው መቀጣት አለበት። በም 14 ላይ ሕዝቡ ይህን ያደርግ እንደ ነበር ተገልጾአል፤ እዚህ ላይ ማለትም ከቍ 32-36 ግለሰብን በሚመለከት ተጠቅሶአል። *ተለይቶ ይጥፋ፤* የዘፀ 12-15 ማብ ይመ።

15፥32 *በሰንበት ቀን ዕንጨት ሲለቅም፤* ሰንበትን ለሻረ ሰው ቅጣቱ ሞት ነበር (ቍ 36፤ ዘፀ 31፥15፤ 35፥2 ይመ)። ሆን ብሎ የእግዚአብሔርን ስም እንደሚሳደበው ሰው ሁሉ (ዘሌ 24፥10-16)፣ ሰንበትን የሻረውም በትዕቢትና በዐመፅ ኀጢአትን በመፈጸሙ (የቍ 30 ማብ ይመ) ሞት ይፈረድበት ነበር። ክር ስቶስ በምድር በነበረበት ጊዜ ከሕዝቡ ፍላጐት ይልቅ ለሰን በት ሕግ ከፍተኛ ግምት እስከሚሰጠው ድረስ ሰንበት በተሳሳተ ሁኔታ እንዲከበር ይደረግ ነበር። በዚህ ጕዳይ ላይ ኢየሱስ ፈሪሳ ውያንን ብዙ ጊዜ ተቃውሞአቸዋል (ማቴ 12፥1-14 ይመ)፤ በእነ ርሱ አመለካከት ኢየሱስን ለመግደል እንዲነሣሡ (ማቴ 12፥14) በቂ ምክንያት የሆኑአቸው እነዚህ ሕጎች ናቸው (ቍ 32-36)።

15፥38 *በየልብሳችሁ ጫፍ ላይ ዘርፍ አድርጉ፤* አንድ ሰው በሚሄድበት ጊዜ በልብሱ ጫፍ ላይ ያለው ዘርፍ ይዞር ነበር (ከቍ 39 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህም የእግዚአብሔርን ትእዛዝ እንዲፈጽሙ ለማስታወስ (ከዘዳ 6፥4-9 ጋር ያነጻጽሩ) እንደ መማ ጸኛ ሆኖ ያገለግል ነበር።

15፥41 *ያወጣኋችሁ እኔ አምላካችሁ እግዚአብሔር ነኝ፤* እግዚአብሔር ሕዝቡ እንዲፈጽሙት የሰጠው ትእዛዝ በማዳን ሥራው ላይ የተመሠረተ ነበር (ዘዳ 20፥2 እና ማብ ይመ)።

*16፥1-7፤* ቀደም ሲል ማርያምና አሮን የሙሴን መሪነት በመቃወም ዐመፅ ለማነሣሣት ሞክረው ነበር (ም 12)። በዚህ ጊዜ ደግሞ ቆሬና ግብረ አበሮቹ የሙሴንና የአሮንን መሪነት በመ ቃወም ተነሡ። ቆሬ በቀዓት በኩል የሌዊ የልጅ ልጅ ነበር። ቀዓ ታዊ በመሆኑ በማደሪያው ውስጥ በሚደረገው የእግዚአብሔር አገልግሎት (4፥1-20 ይመ) ቆሬ ከፍተኛ ኀላፊነት ነበረው። በዚ ህም ላይ ተጨማሪ ሥልጣን ለመያዝ ፈለገ፤ ምኞቱም ካህን ለመ ሆን ነበር፤ ምኞቱን እውን ለማድረግ አታሏል። ከቆሬ ጋር የተባ በሩት ከሮቤል ልጆች ዳታን፣ አቤሮንና ሌሎች እነርሱን የመሳ ሰሉት ሲሆኑ እንዲሁም ወደ ሁለት መቶ አምሳ የሚጠጉ የግል ቂም የነበራቸው ሌሎች የእስራኤል መሪዎችም ነበሩ። ያቀረቡ ትም ክስ ማኅበሩ ሁሉ ቅዱስ ሲሆን (ቍ 3) ሙሴ በሕዝቡ ሁሉ ላይ የመንፈሳዊ መሪነቱን ቦታ በመያዙ፣ "ከመጠን በላይ አብዝቶታል" (ቍ 3) የሚል ነበር። ለዚህ ስድብ አዘል የሐሰት ክስ ሙሴ፣ "ከልክ ያለፋችሁትስ እናንተ ናችሁ!" (ቍ 7) ሲል በቍጣ መለሰ፤ በእሳት የሚቀርብ መሥዋዕትም አዘጋጀ።

ውያን ማኅበረ ሰብ መለየቱና *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ማደሪያ አገልግሎት እንድትፈጽሙ ወደ ራሱ ማቅረቡ፣ እንድታገለግሏቸውም በማ ኅበረ ሰቡ ፊት እንድትቆሙ ማድረጉ አይ በቃችሁምን? [10]አንተንና ከአንተም ጋር ወገ ኖችህ የሆኑትን ሌዋውያንን ሁሉ ወደ ራሱ አቅርቧችኋል፤ እናንተ ግን የክህነቱንም ሥራ ደርባችሁ ለመያዝ ይኸው ትሯሯጣላችሁ:: [11]አንተና ተከታዮችህ ሁሉ አባሪ ተባባሪ ሆና ችሁ የተነሣችሁት *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ላይ ነው፤ ለመሆኑ ታጕረመርሙበት ዘንድ አሮን ማነው?"

[12]ከዚያም ሙሴ የኤልያብን ልጆች ዳታ ንና አቤሮንን አስጠራቸው፤ እነርሱ ግን እንዲህ አሉ፤ "እኛ አንመጣም! [13]በምድረ በዳ ልትገድለን ማርና ወተት ከምታፈሰው ምድር ያወጣኸን አይበቃህም? አሁን ደግሞ በእኛ ላይ ጌታ መሆን ያምርሃል? [14]ከዚ ህም በቀር አንተ ማርና ወተት ወደምታ ፈሰው ምድር አላመጣኸንም፤ ወይም ዕርሻ ዎችንና የወይን ተክል ቦታዎች አላወረስ ከንም:: ታዲያ የእነዚህን ሰዎች ዐይን ታወ ጣለህን?[a] በጭራሽ አንመጣም!"

[15]ሙሴም በጣም ተቈጣ፤ *እግዚአብሔር ንም* (ያህዌ) "ቍርባናቸውን አትቀበል፤ እኔ ከእነዚህ ሰዎች የወሰድኩት አንድ አህያ እንኳ የለም፤ አንዳቸውንም አልበደልሁም" አለ::

[16]ሙሴም ቆሬን እንዲህ አለው፤ "አንተና ተከታዮችህ እንዲሁም አሮን ነገ *በእግዚአ ብሔር* (ያህዌ) ፊት ትቀርባላችሁ:: [17]እያንዳን ዱም ሰው ጥናውን ይወስዳል፤ ባጠቃላይ ሁለት መቶ አምሳ ጥናዎች ይሆናሉ፤ በዚያም ላይ ዕጣን ጨምሮ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ያቀርባል፤ አንተና አሮንም ጥናዎቻ ችሁን እንደዚሁ ታቀርባላችሁ:: [18]እያንዳንዱ ሰው ጥናውን በመያዝ ፍም አድርጎበት፣ ዕጣን ጨምሮበት ከሙሴና ከአሮን ጋር በመገና ኛው ድንኳን ደጃፍ ቆመ:: [19]ቆሬም እነ ርሱን በመቃወም ተከታዮቹን ሁሉ በመገ ናኛው ድንኳን ደጃፍ በሰበሰባቸው ጊዜ፣ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ክብር ለመላው ማኅበር ተገለጠ:: [20]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [21]"ሁሉንም በአ ንድ ጊዜ እንዳጠፋቸው እናንተ ከዚህ ማኅ በር ተለዩ::"

[22]ሙሴና አሮን ግን በግንባራቸው ተደፍ ተው፣ "የሰብአዊ ፍጡር ሁሉ መንፈስ ስም ላክ (ኤሎሂም) የሆንህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሆይ፤ አንድ ሰው ኀጢአት በሠራ በመላው ማኅ በር ላይ ትቈጣለህን?" ሲሉ ጮኹ::

[23]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [24]"ማኅበሩን 'ከቆሬ፣ ከዳ ታንና ከአቤሮን ድንኳኖች ራቁ' በላቸው::"

[25]ሙሴ ተነሥቶ ወደ ዳታንና አቤሮን ሄደ፤ የእስራኤልም ሽማግሌዎች ተከተሉት:: [26]እር ሱም፣ "ከእነዚህ ክፉ ሰዎች ድንኳን ራቍ! የእነርሱ የሆነውን ማንኛውንም ነገር አት ንኩ፤ ያለበለዚያ በእነርሱ ኀጢአት ሁሉ እናንተም ትጠፋላችሁ" ሲል ማኅበሩን አስጠነ ቀቀ:: [27]ስለዚህ እነርሱ ከቆሬ፣ ከዳታንና ከአቤሮን ድንኳን ራቁ:: ዳታንና አቤሮን ወጥተው ከሚስቶቻቸው፣ ከልጆቻቸውና ከሕ ፃናቶቻቸው ጋር በየድንኳኖቻቸው ደጃፍ ላይ ቆመው ነበር::

[28]ሙሴም እንዲህ አለ፤ "እነዚህን ነገሮች ሁሉ እንዳደርግ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደ ላከኝና ከራሴም እንዳይደለ በዚህ ታውቃላ ችሁ፤ [29]እነዚህ ሰዎች እንደማንኛውም ሰው አሟሟት የሚሞቱ ቢሆኑና በሌሎች ሰዎች ላይ የሚደርሰው ብቻ የሚደርስባቸው ከሆነ፣ እኔን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) አልላከኝም:: [30]ይሁን እንጂ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ፈጽሞ አዲስ የሆነ ነገር አምጥቶ ምድር አፏን ከፍታ እነር ሱንና የእነርሱ የሆነውን ሁሉ ብትውጥና በሕይወታቸው ወደ መቃብር[θ] ቢወርዱ፣ ሰዎቹ እግዚአብሔርን (ያህዌ) የናቁ መሆናቸ ውን የምታውቁት ያን ጊዜ ነው::"

[31]ይህን ሁሉ ተናግሮ እንደ ጨረሰ የቆ ሙባት ምድር ተሰነጠቀች፤ [32]አፏንም ከፍታ ሰዎቹን ከነቤተ ሰቦቻቸው እንዲሁም የቆሬን ሰዎች በሙሉ፣ ንብረታቸውንም ሁሉ ዋጠች::

16፥9 ዘፍ30፥15፤ ዘኍ3፥6፤ዘዳ10፥8፤17፥12፤21፥5፤1ሳሙ2፥11፤መዝ134፥1፤ሕዝ44፥11
16፥10 ዘኍ3፥10፤18፥7፤መሳ17፥5:12
16፥11 ቍ41፤ዘፀ16፥7፤1ቆሮ10፥10
16፥12 ቍ1:14:27
16፥13 ዘፍ13፥8፤ዘኍ13፥27፤14፥2፤ሐሥ7፥27:35
16፥14 ቍ12፤ዘፀ22፥5፤23፥11፤ዘሌ20፥24፤23፥11፤ዘኍ20፥5፤መሳ16፥21፤1ሳሙ11፥2፤1ነገ14፥25፤ነህ13፥15፤መዝ105፥33፤ኤር5፥17፤39፥7፤ሆሴ2፥12፤ኢል2፥22፤ሐጌ2፥19፤ዘካ3፥10
16፥15 ዘፀ4፥14፤1ሳሙ12፥3
16፥16 ቍ6
16፥17 ሕዝ8፥11
16፥18 ዘሌ10፥1
16፥19 ቍ42፤ዘፀ16፥7፤ዘኍ14፥10፤20፥2፥6
16፥21 ቍ24፤ዘፍ19፥14፤ዘፀ32፥10
16፥22 ዘፍ18፥23፤ዘሌ10፥6፤ዘኍ14፥5፤27፥16፤ኢዮ12፥10፤21፥20፤27፥8፤33፥4፤34፥14፤ኤር32፥27፤ሕዝ18፥4፤ዕብ12፥9
16፥25 ዘፀ19፥7
16፥26 ዘፍ19፥15፤ኢሳ52፥11፤ኤር51፥6
16፥27 ቍ12:32፤ዘፀ33፥8፤ኢሱ7፥24፤ኢሳ13፥16፤14፥21
16፥28 ዘፀ3፥12፤1ነገ18፥36፤ዮሐ5፥36፤6፥38
16፥29 ዘኍ24፥13፤ኢዮ31፥2፤መክ3፥19
16፥30 ቍ33፤ዘፍ37፥35፤ዘኍ14፥11፤1ሳሙ2፥6፤ኢዮ5፥26፤21፥13፤መዝ9፥17፤16፥10፤55፥15፤141፥7፤ኢሳ5፥14፤14፥11፤38፥18፤ሕዝ26፥20
16፥31 ኢሳ64፥1-2፤ሕዝ47፥1-12፤ሚክ1፥3-4፤ዘካ14፥4
16፥32 ዘፀ15፥12

[a]14 ባሪያ ታደርጋቸዋለህ፤ ወይም ታታላቸዋለህ ማለት ነው::
θ30 በዕብራይስጥ ሲኦል ማለት ነው::

16፥12 *ዳታንና አቤሮን*፤ በሙሴ ላይ ክስ ያቀረቡት ወደ ተስፋዪቱ ምድር አላስገባንም በሚል ሰበብ ነበር:: ሙሴ ሕዝቡን "ማርና ወተት ከምታፈሰው ምድር" (ቍ 13) አስወጥቶናል በማ ለት ሕዝቡን የሚያደናግር ማስረጃ በማቅረብ ተናግረዋል:: ይሁን እንጂ እውነት ባልሆነ ፈጠራ በአእምሮአቸው ውስጥ ተቀርጾ የታያቸው የግብፅ ምድር፣ እስር ቤት ከመሆን ይልቅ ወደ ገነት መለወጧ ነበር::

16፥15 *አንዳቸውንም አልበደልሁም*፤ ሙሴ በሰብአዊ ስሜት ምንም በደል አለመፈጸሙን መናገሩ፣ ምን ያህል ትሑት እንደ ነበር ያመለክታል::

*16፥18-21፤* መሥዋዕት የማቅረቡ ፉክክሮሽ የተካሄደው በእሳት ነበር፤ እግዚአብሔር ቅዱስ በሆነው ማደሪያ ውስጥ የእ ርሱ ካህናት አድርጎ የሚቀበላቸው የትኞቹን ሰዎች ይሆን? ከቆሬ ጋር ያበሩት ሁለት መቶ አምሳ ሰዎች፣ በመገናኛው ድንኳን መግ ቢያ ላይ ሙሴንና አሮንን ለመቃወም በትዕቢት ተሞልተው መጡ:: በዚያ የእግዚአብሔር ክብር መገለጡ የማይቀር ሲሆን፣ ይኸው ዐመፀኞችን ሰዎች (ቍ 21) በሞት የሚቀጣ ቅጽበታዊ ቃል የያዘ በድንገት የሆነ ቅጣት ነበር (ቍ 19)፤ ቅጣቱም የተገ ላቢጦሽ ሆነ:: በጥናዎቻቸው ውስጥ እሳት በማድረግ በእግዚአ ብሔር ፊት ራሳቸውን እንደ ካህን ለማቅረብ የደፈሩት እነዚያ ሁለት መቶ አምሳ ሰዎች፣ በእግዚአብሔር እሳት ተቃጥለው ሞቱ (ቍ 35)

*16፥22፤* ሙሴና አሮን ወደ እግዚአብሔር በመማጸናቸው እሳቱ ቆመ እንጂ ሕዝቡ ሁሉ ሊጠፉ ነበር::

16፥24 *ራቁ!* እግዚአብሔር የሚሰጠው ፍርድ እጅግ ከባድ ነው፤ ነገር ግን ቆመው ተመልካች የነበሩትንና ከጥፋተኞቹ ጋር ያላበሩትን ሰዎች ማጥፋት አልፈለገም:: በዚህ ስፍራ ላይ ቆሬ ከሁለት መቶ አምሳዎቹ ሐሰተኛ ካህናት ተለይቶ በሙሴ ላይ የጀመሩትን ተቃውሞ ለመቀጠል ከዳታንና ከአቤሮን ጋር አብሮ የቆመ ይመስላል::

16፥30 *አዲስ የሆነ ነገር*፤ በፍጥነት የሚፈጸመው ይህ ፍርድ በእግዚአብሔር የሚሆን እንጂ በሌላ ነገር ወይም መንገድ ተተ ርጕሞ በአጋጣሚ የሚደረግ ያለመሆኑን ሙሴ ለሕዝቡ በሚገባ አረጋግጦአል:: ዐመፀኞችን ለመዋጥ ምድር መሰንጠቋ፣ የሙሴ ንና የአሮንን እውነተኛነትና የእግዚአብሔርን ቍጣ የሚያሳይ ትክክለኛ ምልክት ነበር::

16፥32 *ከነቤተ ሰቦቻቸው... ዋጠች*፤ የቆሬ ልጆች ማስተ ዋል በጐደለው በአባታቸው ምክር ውስጥ ስላልገቡ ከእርሱ ጋር

33እነርሱም ካላቸው ከማናቸውም ነገር ጋር ከነሕይወታቸው ወደ መቃብር ወረዱ፤ ምድሪቱም በላያቸው ተከደነችባቸው፤ ጠፉ፤ ከማኅበረ ሰቡም ተወገዱ። 34ከጩኸታቸውም የተነሣ በአካባቢያቸው የነበሩት እስራኤላውያን ሁሉ፣ "ምድሪቱ እኛንም እኮ ልትውጠን ነው" ብለው ሸሹ።

35እሳትም *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘንድ ወርዶ የሚያጥኑትን ሁለት መቶ አምሳ ሰዎች በላቻቸው።

36*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ 37"ጥናዎቹ የተቀደሱ ናቸውና ከተቃጠሉት ሰዎች ዘንድ ወስደህ በውስጣቸው ያለውን ፍም አርቆ እንዲደፋ ለካህኑ ለአሮን ልጅ ለአልዓዛር ንገረው፤ 38እነዚህም ሕይወታቸውን ለማጥፋት ኀጢአት የሠሩ ሰዎች ጥና ናቸው፤ ጥናዎቹም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት የቀረቡና የተቀደሱ በመሆናቸው ለመሠዊያው መለበጫ እንዲሆኑ ቀጥቅጠህ አሣሣቸው፤ እነዚህም ለእስራኤላውያን ማስጠንቀቂያ ይሁኑ።"

39ከዚህ የተነሣም ካህኑ አልዓዛር የተቃጠሉት ሰዎች አምጥተዋቸው የነበሩትን የናስ ጥናዎች ሰብስቦ የመሠዊያው መለበጫ እንዲሆኑ ቀጠቀጣቸው፤ 40ይህን ያደረገውም፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሙሴ አማካይነት ባዘዘው መሠረት ነው፤ ይህም ከአሮን ዘር በስተቀር ማንም ሰው *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ቀርቦ ዕጣን እንዳያጥን ያለበለዚያ ግን፣ እንደ ቆሬና እንደ ተከታዮቹ እንደሚሆን ለእስራኤላውያን የተሰጠ ማስጠንቀቂያ ነበር።

41በማግሥቱም መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ፣ "እናንተ *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ሕዝብ ገድላችኋል" በማለት በሙሴና በአሮን ላይ አጒረመረሙ።

42ማኅበሩም ሙሴንና አሮንን ለመቃወም በተሰበሰቡ ጊዜ ወደ መገናኛው ድንኳን ዘወር ሲሉ ደመና ድንኳኑን በድንገት ሸፍኖት አዩ፤ *የእግዚአብሔርም* (ያህዌ) ክብር ተገለጠ። 43ከዚያም ሙሴና አሮን ወደ መገናኛው ድንኳን ፊት ለፊት ሄዱ። 44*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ 45"በቅጽበት አጠፋቸዋለሁና ከዚህ ማኅበር ራቅ" እነርሱም በግንባራቸው ተደፉ።

46ከዚያም ሙሴ አሮንን፣ "*ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘንድ ቊጣ ወጥቶ መቅሠፍት ጀምሮአልና ጥናውን ወስደህ ዕጣን በመጨመር ከመሠዊያው እሳት አድርግበት፤ ፈጥነህም ወደ ማኅበሩ ሄደህ አስተሰርይላቸው" አለው። 47ስለዚህ አሮን፣ ሙሴ በነገረው መሠረት ወደ ማኅበሩ መካከል ሮጦ ገባ፤ መቅሠፍቱም ቀደም ብሎ በሕዝቡ መካከል መስፋፋት ጀምሮ ነበር፤ ሆኖም አሮን ዕጣኑን ዐጥኖ አስተሰረየላቸው። 48እርሱም በሕይወት ባሉትና በሞቱት መካከል ቆመ፤ መቅሠፍቱም ተከለከለ። 49ይሁን እንጂ በቆሬ ምክንያት የሞቱትን ሳይጨምር ዐሥራ አራት ሺህ ሰባት መቶ ሰዎች ተቀሥፈው ሞቱ። 50ከዚያም መቅሠፍቱ ቆመ፤ አሮንም ሙሴ ወዳለበት ወደ መገናኛው ድንኳን ደጃፍ ተመለሰ።

## የአሮን በትር ማቈጥቈጥ

**17** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ 2"ለእስራኤላውያን ንገራቸውና ከየነገዱ አለቆች አንዳንድ፣ ባጠቃላይ ዐሥራ ሁለት በትር ተቀበል፤ የያንዳንዱንም ሰው ስም በየበትሩ ላይ ጻፈው። 3ለያንዳንዱ የነገድ አለቃ አንዳንድ በትር መኖር ስላለበት በሌዊ በትር ላይ የአሮንን ስም ጻፍ። 4በትሮቹንም እኔ ከአንተ ጋር በምገናኝበት በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከምስክሩ ፊት ለፊት አስቀምጣቸው። 5እኔ የምመርጠው ሰው በትርም ታቈጠቊጣለች፤ እስራኤላውያን በእናንተ ላይ ነጋ ጠባ የሚያደርጉትንም ማጒረምረም በዚህ እገታለሁ።"

6ሙሴም ለእስራኤላውያን ተናገራቸው፤ አለቆቻቸውም በቀደሙት በያንዳንዱ አባቶች ስም ዐሥራ ሁለት በትር ሰጡት፤ የአሮን በትርም በበትሮቹ መካከል ነበረች። 7ሙሴም በትሮቹን ወስዶ በምስክሩ ድንኳን ውስጥ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት አኖራቸው።

16፥33 ቍ30፤ መክ9፥10
16፥35 ዘሌ10፥2፤ ዘኍ11፥1-3፤26፥10፤ ራእ11፥5
16፥37 ቍ6፤ዘፀ 6፥23
16፥38 ዘፀ20፥24፤ 38፥1-7፤ዘሌ10፥1፤ ዘኍ26፥10፤ዘጸ28፥46 ፤ምሳ20፥2፤ኤር44፥ 29፤ሕዝ14፥8፤ 2ጴጥ2፥6
16፥39 ዘሌ20፥14፤ 2ዜና26፥18
16፥40 ዘፀ30፥1፡9፤ ዘኍ3፥102ኛዜና26፥ 18፤2ነገ12፥3፤2ዜና2 6፥18፤ኢሳ1፥13፤ 66፥3፤ኤር41፥5፤ 44፥3
16፥42 ቍ19፤ዘፀ 16፥7፤ዘኍ14፥10
16፥45 ዘፀ32፥10
16፥46 ዘፀ29፥36፤ ዘሌ10፥1፡6፤26፥25፤ ዘኍ1፥53፤8፥19፤መዝ 106፥29
16፥47 ዘኍ25፥6-8
16፥48 ዘኍ25፥8፤ መዝ106፥30
16፥49 ቍ32
17፥2 ዘፍ32፥10፤ ዘፀ4፥2፤ዘኍ1፥4
17፥3 ዘኍ1፥3
17፥4 ቍ7፤ዘፀ 16፥34፤25፥22፤40፥2
17፥5 ቍ8፤ዘፀ 16፥7፤ዘኍ16፥5
17፥7 ዘፀ38፥21

አልሞቱም ነበር (26፥11)። ነገር ግን ሌሎቹ ዐመፀኞችና ቤተ ሰቦቻቸውም ከእነርሱ ጋር አብረው ሞቱ።

16፥37 *ጥናዎቹ … ወስደህ* እውነተኞቹ ካህናት፣ ሁለት መቶ አምሳዎቹ ሐሰተኞች ሰዎች ተቃጥለው ከሞቱበት ቦታ ከናስ የተሠሩት ጥናዎቻቸውን በመውሰድ ከጠፈጠፉአቸው በኋላ ካህን ሳይሆን ራሱን ካህን አድርጎ ለሚቈጥር ማስተዋል ለጐደለው ሰው (ቍ 40) ማስጠንቀቂያ ይሆኑ ዘንድ ለመሠዊያ መለበጫ አደረጉአቸው።

16፥41 *መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ … አጒረመረሙ፤* ለሞቱት ሰዎች ተጠያቂ አድርገው ሙሴን ያለአግባብ በመክሰስ ማኅበሩ ሁሉ እርሱን ተቃወመ። ሙሴና አሮን ጣልቃ ገብተው በግንባራቸው ተደፍተው በመማለድ የእግዚአብሔርን ቍጣ ባያበርዱ ኖሮ (ቍ 4፥22 ይመ) ተደጋግሞ በታየው ዐመፃቸው ምክንያት (ቍ 45 ይመ) ጠቅላላው ሕዝብ በጠፋ ነበር።

16፥49 *ዐሥራ አራት ሺህ ሰባት መቶ ሰዎች… ሞቱ፤* የማኅበሩ ጠቅላላ ቍጥር ቢምዕራፍ ሁለት ላይ በተጠቀሰው የሕዝብ ቈጠራ ዝርዝር መሠረት ከሆነ እዚህ ላይ የተጠቀሰው የሕዝብ ብዛት ተቀባይነት ያለው ይሆናል።

*17፥1-13፤* በዚህ ክፍል የተጠቀሰው ታሪክ የተፈጸመው፣ በቆሬ ላይ ከተሰጠው መለኮታዊ ፍርድ (16፥1-35)፣ የዐመፀኞቹ ሰዎች ጥናዎችና ከእነርሱም ጋር ተያይዞ የተደረገው ነገር (16፥36-50) ያስገኘው ምሳሌያዊ ትምህርትን በተመለከተ ከተጻፈው ትረካ በኋላ ነው። በዚያ ሁሉ ተቃውሞ የአሮን ክህነት የጸደቀና የተረጋገጠ መሆኑን የሚያመለክቱ ተከታታይ ታሪኮችን በመያዝ አንጻር ም 17 ሦስተኛ መሆኑ ነው። ከየነገዱ አንዳንድ በትር መወሰዱና ዐሥራ ሁለት በትሮች መመረጣቸው የአሮንን መለኮታዊ ምርጫ በድጋሚ አረጋግጦ ለማመልከት የገባ ምሳሌያዊ አገላለጽ ነበር።

17፥3 *በሌዊ በትር ላይ የአሮንን ስም ጻፍ፤* እግዚአብሔር የሌዊን ነገድ አገልጋዮች አድርጎ መምረጡና በተለይም አሮንን ካህን ማድረጉ በም 17 ላይ መከላከያ የሚሆን ታሪክ ተፈጽሞአል። እግዚአብሔርም ምርጫው ትክክል መሆኑን ለማሳየት ታምር አድርጎአል (ቍ 8 ይመ)፤ የቆሬ ዐመፅ በብዙዎች የተደገፈ ስለ ነበር፣ ለማረጋገጫ የሚደረገው ታምር ግልጽና የማያሻማ መሆን ነበረበት። ከቆሬ ጋር ያበሩት ሁለት መቶ አምሳ ሰዎች፣ ከብዙ ነገድ ምናልባትም ከሁሉም ነገድ የመጡ ሊሆኑ ይችላሉ።

17፥4 *ከምስክሩ ፊት ለፊት፤* ዐሥርቱ ትእዛዛትን በያዘው በታቦቱ ፊት ለፊት ማለት ነው፤ ምናልባትም በዕጣን መሠዊያው አጠገብ ባለው ቅዱስ ስፍራ ሊሆን ይችላል።

[8]በማግስቱ ሙሴ ወደ ምስክሩ ድንኳን ሲገባ በሌዊ ቤት ስም የቀረበችው የአሮን በትር ማቈጥቈጥ ብቻ ሳይሆን እንቡጥ አውጥታ፣ አብባና ለውዝ አፍርታ አገኛት። [9]ከዚያም ሙሴ በትሮቹን ከእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት አውጥቶ ወደ እስራኤላውያን ሁሉ አመጣቸው፤ እነርሱም አዩ፤ እያንዳንዱም ሰው የየራሱን በትር ወሰደ።

[10]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "የአሮን በትር ለዐመፀኞቹ ምልክት እንድትሆን መልሰህ በምስክሩ ፊት ለፊት አኑራት፤ እነርሱ እንዳይሞቱም በእኔ ላይ የሚያደርጉትን ማጕረምረም ይህ ይገታዋል" አለው። [11]ሙሴም ልክ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘው አደረገ።

[12]ከዚያም እስራኤላውያን ሙሴን እንዲህ አሉት፤ "እነሆ መሞታችን ነው! ጠፋን፤ ሁላችንም መጥፋታችን ነው! [13]ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ማደሪያ የሚጠጋ እንኳ ማንኛውም ሰው ቢሆን ይሞታል፤ ሁላችንም ልንጠፋ ነው እንዴ?"

## የካህናትና የሌዋውያን ተግባር

**18** እግዚአብሔር (ያህዌ) አሮንን እንዲህ አለው፤ "መቅደሱን በተመለከተ ስለሚፈጸም በደል አንተ፣ ልጆችህና የአባትህ ቤተ ሰቦች ኀላፊነቱን ትሸከማላችሁ፤ ክህነቱን በተመለከተ ስለሚፈጸም በደል ግን ኀላፊነቱ የሚወድቀው በአንተና በልጆችህ ላይ ብቻ ነው። [2]አንተና ልጆችህ በምስክሩ ድንኳን ፊት በምታገለግሉበት ጊዜ አብረዋችሁ እንዲሆኑና እንዲረዱአችሁ ከአባትህ ነገድ ሌዋውያንን አምጣቸው። [3]እነርሱም በአንተ ኀላፊነት ሥር ሆነው የድንኳኑን አገልግሎት በሙሉ ያከናውኑ፤ ይሁን እንጂ ወደ መቅደሱ ዕቃዎችም ሆነ ወደ መሠዊያው አይጠጉ፤ ከተጠጉ ግን እነርሱም አንተም ትሞታላችሁ። [4]እነርሱም የመገናኛውን ድንኳን ለመንከባከብ ማለትም በድንኳኑ ውስጥ የሚሠራውን ሥራ ሁሉ ኀላፊነት በመውሰድ አብረዋችሁ ይሁኑ፤ ከዚህ በተረፈ ግን እናንተ ወዳላችሁበት ማንም ሰው አይጠጋ።

[5]"በእስራኤላውያን ላይ ዳግም ቍጣ እንዳይደርስባቸው የመቅደሱና የመሠዊያው እንክብካቤ ኀላፊነት የሚመለከተው እናንተን ይሆናል። [6]ከእስራኤላውያን መካከል ወገኖቻችሁን ሌዋውያንን ለእናንተ ስጦታ አድርጌ እኔ ራሴ መርጫቸዋለሁ፤ በመገናኛው ድንኳን ውስጥ የሚከናወነውን ሥራ ሁሉ እንዲሠሩ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የተሰጡ ናቸው። [7]ይሁን እንጂ በመሠዊያው ላይ የሚደረገውንና በመጋረጃ ውስጥ ያለውን ማንኛውንም የክህነት አገልግሎት የምትፈጽሙት አንተና ልጆችህ ብቻ ናችሁ፤ የክህነቱን አገልግሎት ስጦታ አድርጌ ሰጥቻችኋለሁ። ከእናንተ በስተቀር ወደ መቅደሱ የሚጠጋ ቢኖር ግን ይገደል።"

## ለካህናትና ለሌዋውያን የሚሰጡ መባዎች

[8]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) አሮንን እንዲህ አለው፤ "ለእኔ በሚቀርበው መባ ላይ ኀላፊነትን የሰጠሁህ እኔው ራሴ ነኝ፤ እስራኤላውያን የሚያቀርቡልኝም የተቀደሰ መባ ሁሉ ለአንተና ለልጆችህ መደበኛ ድርሻችሁ እንዲሆን ሰጥቻችኋለሁ። [9]ለእኔ ከሚቀርብልኝ እጅግ ከተቀደሰው መባ ሁሉ፣

17፥8 ቍ2:7:10፤ ዘኍ1፥50፤ሕዝ 17፥24፤ዕብ9፥4
17፥9 ቍ2
17፥10 ቍ8፤ዘፀ 23፥21፤ዘዳ9፥24፤መዝ 66፥7፤68፥18፤ምሳ 24፥21
17፥12 መሳ13፥22፤ ኢሳ6፥5፤15፥1
17፥13 ዘኍ1፥51
18፥1 ዘፀ28፥38
18፥2 ዘኍ3፥10
18፥3 ቍ7፤ዘኍ 1፥51፤3፥32
18፥4 ዘኍ3፥38
18፥5 ቍ3፤ዘሌ6፥12
18፥6 ዘኍ3፥8:9
18፥7 ቍ3:20፤ዘፀ 29፥9፤40፥13፤ዘኍ 3፥10፤ዕብ5፥4፤9፥3:6
18፥8 ዘፀ18፥1፤ ዘሌ2፥2፤6፥16፤7፥6:3 1-34:36፤ዘዳ 18፥1፤2ዜና31፥4
18፥9 ዘሌ2፥1፤ 5፥15፤6፥17:25

17፥8 *ማቈጥቈጥ ብቻ ሳይሆን እንቡጥ አውጥታ፣ አብባና ለውዝ አፍርታ አገኛት፤* ማን ምን እንዳደረገ፣ የድርጊቱ ዐላማ ምን እንደ ሆነ በማያሻማ ሁኔታ ግልጽ ይሆን ዘንድ እግዚአብሔር በበትሯ ላይ የተለያዩ ለውጦች እንዲታዩ አደረገ።

17፥10 *በምስክሩ ፊት ለፊት፤* የአሮን በትር በቃል ኪዳኑ ታቦት ውስጥ ወይም አጠገብ (ዕብ 9፥4 ይመ)፣ ካሉት የሙሴን ሕግ ከያዘው ጽላት (የዘፍ 25፥16 ማብ ይመ) እና መና ከያዘው ማድጋ (ዘፀ 16፥33-34) ጋር ሆነች። ስለ ሕዝቡ ላደረገው የተለየ ነገር መታሰቢያ ይሆን ዘንድ እነዚህ ቅዱስ ምሳሌዎች ሁል ጊዜ በእግዚአብሔር ፊት ነበሩ። በተጨማሪም በሚቀጥለው ትውልድ ማንም ሰው በእግዚአብሔር አገልግሎት ውስጥ የተለየና ቅዱስ የሆነውን የአሮንን የክህነት ሥልጣን መጠየቅ ቢደፍር እግዚአብሔር አሮንን መምረጡን የሚያመለክተው ይህ መታሰቢያ የሰውየውን የድፍረት ጥያቄ የሚቃወም ይሆናል። በእስራኤል የአምልኮ ሥርዐት ውስጥ (የ18፥1-7 ማብ ይመ) የአሮንንና የልጆቹን አገልግሎት አስፈላጊነት ከተሰጣቸው ኀላፊነት በላይ አድርጎ መገመትም አስቸጋሪ ሁኔታ ውስጥ ያስገባል።

17፥12 *መሞታችን ነው!* የአሮንን ክህነት በመቃወም ያሳዩት ዐመፅ በመጨረሻ ላይ ኀጢአት እንደ ሆነ ሕዝቡ ማስተዋሉን ያመለክታል። ወደ እግዚአብሔር ለመቅረብ የሚያስችሉ ተገቢ መንገዶች በም 18-19 በሰፋት ተገልጸዋል።

*17፥12-13፤* ሕዝቡ ያሰማው ወዮታ ትክክለኛ ነው፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የሚገኝበትን ቅዱስ ሥፍራ የሚያረክስ ከባድ ኀጢአት መፈጸም በሞት የሚያስቀጣ ነበር። እግዚአብሔር ያደረገው ቸርነት የጸጋው አንዱ ገጽታ ነበር (ከመዝ 99፥6-8 ጋር ያነጻጽሩ)፤ በመሠረቱ ሕዝቡ ከፍርድ ነጻ ለመሆን ተስፋ የሚያደርገው ይህን ብቻ ነበር።

*18፥1-7፤* በእግዚአብሔር የተመረጡት አሮንና ቤተ ሰቡ ለተቀደሰው አምልኮ ትክክለኛ ካህናት ይሆኑ ዘንድ የተሰጣቸው ኀላፊነት እጅግ ከባድ ነበር። በ17፥12-13 ሕዝቡ ያሰማው ወዮታ ትክክለኛ ነው፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የሚገኝበትን ቅዱስ ሥፍራ የሚያረክስ ከባድ ኀጢአት መፈጸም በሞት የሚያስቀጣ ነበር። እግዚአብሔር ሕጋዊ የሆነ ክህነት በመስጠት ያደረገው ቸርነት የጸጋው አንዱ ገጽታ ነበር (ከመዝ 99፥6-8 ጋር ያነጻጽሩ)፤ በመሠረቱ ሕዝቡ ከፍርድ ነጻ ለመሆን ተስፋ የሚያደርገው ይህን ብቻ ነበር።

18፥1 *ስለሚፈጸም በደል ... ኀላፊነቱን ትሸከማላችሁ፤* ካህናትና ሌዋውያን በእግዚአብሔር ማደሪያ ውስጥ ለሚፈጸም ርኩሰት ሁሉ ተጠያቂዎች ናቸው፤ እግዚአብሔርን ለማገልገል፣ ፈቃዱንም ለመፈጸም ከፍተኛ ጥንቃቄ ማድረግ ይገባቸው ነበር (ከዘሌ 10፥7 ጋር ያነጻጽሩ)።

18፥2 *ሌዋውያንን አምጣቸው፤* ከሌዊ ነገድ የሆኑት ሌሎች ሰዎች ከአሮን ወገን የሆኑትን ካህናት ሊያግዙአቸው ይገባል፤ እነዚህ ረዳቶች ከተወሰነላቸው አገልግሎት ውጭ አልፈው መሄድ አይፈቀድላቸውም። ነገር ግን ተላልፈው ከተገኙ የሚሞቱት እነርሱ ብቻ ሳይሆኑ ኀላፊነት የተሰጣቸው ካህናትም ጭምር ነበሩ (ቍ 3)።

18፥7 *የክህነቱን አገልግሎት ስጦታ አድርጌ ሰጥቻችኋለሁ፤* ካህናት ቅዱስ ወደ ሆነው ቦታ ለመቅረብና በእግዚአብሔር ፊት ለማገልገል ከሌሎች ሰዎች ሁሉ ይልቅ ልዩ መብት ሰጥቶአቸው ነበር። ክህነቱ ለካህናቱም ሆነ ለሕዝቡ የእግዚአብሔር ጸጋ ስጦታ ነበር።

18፥8 *ለአንተና ለልጆችህ መደበኛ ድርሻችሁ፤* ካህናቱ በአገልግሎት ሥራቸው ውስጥ ሊታገዙ ይገባ ነበር (ዘሌ 6፥14-7፥36 ይመ)። ሌዋውያን በጠቅላላ፣ በተለይም ካህናት እግዚአብሔር ለሕዝቡ ከሚሰጠው ርስት ድርሻ ስላልነበራቸው የተሰጣቸው ነገር ምን እንደ ሆነ በሚገባ እንዲያውቁት ማድረግ አስፈላጊ ነበር። በምድሪቱ ድርሻ አልነበራቸውም፤ ድርሻቸውና ርስታቸው እግዚአብሔር ራሱ ነበር (ቍ 20)።

በእሳት የማይቃጠለው የራስህ ድርሻ ይሆ
ናል፤ እጅግ የተቀደሰ አድርገው ከሚያ
መጡልኝ ስጦታ ከእህል ቍርባንም ሆነ
ከኀጢአት ወይም ከበደል መሥዋዕት የሚነ
ሣው ሁሉ የአንተና የልጆችህ ድርሻ ነው።
[10]እጅግ ቅዱስ መሆኑን በማሰብ በተቀደሰ
ስፍራ ብላው፤ እያንዳንዱም ወንድ ከዚሁ
ይብላ፤ ይህ ለአንተም የተቀደሰ ነው።

[11]“እስራኤላውያን ከሚያቀርቡት ስጦታ፣ ከሚ
ወዘወዘው ቍርባን ተለይቶ የሚቀመጠው
ስጦታ ሁሉ የአንተ ይሁን። ይህንም ለአ
ንተ፣ ለወንድና ለሴት ልጆችህ መደበኛ ድርሻ
አድርጌ ሰጥቻችኋለሁ። ከቤተ ሰዎችህ በሥ
ርዐቱ መሠረት የነጻ ማንኛውም ሰው ከዚሁ
መብላት ይችላል።

[12]“እስራኤላውያን የመከር በኵራት አድ
ርገው *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚሰጡትን ምርጥ
የወይራ ዘይት በሙሉ፣ ምርጥ የሆነውን
አዲስ የወይን ጠጅና እህል ሁሉ ለእናንተ
ሰጥቻችኋለሁ። [13]*ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚያ
መጡት የምድራቱ በኵር ፍሬ ሁሉ የአንተ
ይሆናል። ከቤተ ሰዎችህ በሥርዐቱ መሠ
ረት ንጹሕ የሆነ ማንኛውም ሰው ይህን
መብላት ይችላል።

[14]“*ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፈጽሞ የተሰጠ[ሐ]
በእስራኤል ያለ ማንኛውም ነገር ሁሉ የአ
ንተ ነው። [15]ማሕፀን የሚከፍትና *ለእግዚአ
ብሔር* (ያህዌ) የተሰጠ ሰውም ሆነ እንስሳ
የአንተ ነው፤ ነገር ግን ማንኛውም በኵር
ሆኖ የተወለደውን ወንድ ልጅና ንጹሕ ካል
ሆነ እንስሳ በኵር ሆኖ የተወለደውን ተባዕት
ሁሉ ዋጀው። [16]እነዚህም አንድ ወር ሲሆና
ቸው ሃያ ጌራ በሚመዝነው በቤተ መቅ
ደሱ ሰቅል[T] ልክ፣ በተወሰነው በማዋጃው ዋጋ
በአምስት ሰቅል ጥሬ ብር ትዋጀዋለህ።

[17]“የተቀደሱ ስለሆኑ የበሬ፣ የበግ ወይም
የፍየል በኵር የሆኑትን አትዋጃቸውም፤ ደማ
ቸውን በመሠዊያው ላይ ትረጨዋለህ፤ ሥባ
ቸውንም ሽታው *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ደስ
የሚያሰኝ እንዲሆን በእሳት የሚቀርብ መሥ
ዋዕት አድርገህ *ታቃጥለዋለህ*። [18]የሚወዘ
ወዘው ቍርባን ፍርምባና የቀኙ ወርች የአ
ንተ እንደ ሆነ ሁሉ የእነዚህም ሥጋ የአ

18፥10 ዘሌ6፥16፡17፡18
18፥11 ዘፀ29፥26፤ ዘሌ7፥30፡31-34፤ 13፥3፡22፥1-16፤ ዘኍ6፥20
18፥12 ዘፍ4፥3፤ዘፀ 23፥19፡34፥26፤ዘፀ 7፥13፡11፥14፡12፥17 ፡28፥51፡2ነገ18፥32፤ 2ዜና31፥5፤ነህ10፥35፡ 37፤ኤር31፥12፤ሕዝ 23፥41፤ሆሴ2፥8፤ኢዩ 1፥10፤ሐጌ1፥11
18፥13 ቍ11፤ ዘፀ29፥27
18፥14 ዘሌ27፥21፤ ኢሱ6፥17-19
18፥15 ዘፍ10፥15፤ ዘፀ13፥2፡13፤ ዘኍ3፥46
18፥16 ዘፀ30፥13፤ ዘሌ27፥6፤ዘኍ3፥15፡47
18፥17 ዘፀ29፥13፤ ዘሌ1፥9፡3፥2፡27፥9
18፥18 ቍ11፤ ዘሌ7፥30
18፥19 ዘሌ2፥13፤ 2ነገ12፥4
18፥20 ቍ24፤ዘኍ 26፥62፤ዘዳ10፥9፡12፥ 12፡14፥27፡18፥1-2፤ ኢሱ13፥33፤ሕዝ 44፥28
18፥21 ቍ24፤ዘፍ 28፥22፤ዘሌ27፥30- 33፤ዘኍ1፥53፡31፥28 ፤ዘዳ14፥22፤ነህ10፥37 ፡13፥5፤ሚል3፥8፤ ዕብ7፥5
18፥22 ዘፀ28፥43
18፥23 ቍ20፤ዘፀ 12፥14፡27፥21፤ዘኍ 10፥8፡26፥62፤ ዘዳ10፥9፤ሕዝ44፥10
18፥24 ዘሌ27፥30፤ ዘዳ26፥12
18፥26 ቍ21፡28፤ ነህ10፥38
18፥27 ቍ12፡30፤ ዘፍ50፥10፤ዘሌ7፥18፤ ዘዳ15፥14፤መሳ6፥37፤ ሩት3፥3፡6፡ 14፤1ሳሙ23፥1

ንተ ይሆናል። [19]እስራኤላውያን *ለእግዚአ
ብሔር* (ያህዌ) ከሚያቀርቡት ከተቀደሰ ቍር
ባን የሚለየው ሁሉ ለአንተ፣ ለወንድና
ለሴት ልጆችህ መደበኛ ድርሻ አድርጌ ሰጥ
ቻችኋለሁ፤ ይህም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት
ለአንተና ለዘሮችህ ዘላለማዊ የጨው ኪዳን
ነው።”

[20]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) አሮንን እንዲህ አለው፤
“ከምድራቸው የምትካፈለው ርስት፣ ከእነር
ሱም የምታገኘው ድርሻ የለህም፤ በእስራኤ
ላውያን መካከል ድርሻህና ርስትህ እኔ ነኝ።

[21]“በመገናኛው ድንኳን በሚያገለግሉበት
ጊዜ ለሚሠሩት ሥራ ደመወዝ እንዲሆና
ቸው ከእስራኤል የሚወጣውን ዐሥራት
ሁሉ ለሌዋውያን ርስት አድርጌ ሰጥቻቸዋ
ለሁ። [22]አድራጎቱ ኀጢአት ስለ ሆነ ሞት
እንዳያስከትልባቸው ከእንግዲህ ወዲያ እስ
ራኤላውያን ወደ መገናኛው ድንኳን አይጠጉ።
[23]በመገናኛው ድንኳን የሚከናወነውን ሥራ
የሚሠሩት ሌዋውያን ናቸው፤ በዚያም ለሚ
ፈጸመው በደል ኀላፊነቱን ይሸከማሉ። ይህም
ለሚመጡት ትውልዶች የዘላለም ሥርዐት
ነው፤ ሌዋውያን በእስራኤላውያን መካከል
ርስት አይሰጣቸውም። [24]በዚህ ፈንታም እስ
ራኤላውያን መባ አድርገው *ለእግዚአብሔር*
(ያህዌ) የሚያቀርቡትን ዐሥራት ለሌዋውያን
ርስት አድርጌ ሰጥቻቸዋለሁ፤ እኔም እነር
ሱን በተመለከተ፣ ‘በእስራኤላውያን መካ
ከል ርስት አይኖራቸውም’ ያልኩት በዚሁ
ምክንያት ነው።”

[25]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤
[26]“ሌዋውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላ
ቸው፤ ‘ርስት አድርጌ የምሰጣችሁን ዐሥራት
ከእስራኤላውያን በምትቀበሉበት ጊዜ፣ እናን
ተም ካገኛችሁት ላይ አንድ ዐሥርኛ በማ
ውጣት *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) መባ አድርጋችሁ
ታቀርባላችሁ። [27]ቍርባናችሁም ከዐውድማ
እንደ ገባ እህል ወይም ከመጭመቂያ እንደ
ወጣ ወይን ሆኖ ይቈጠርላችኋል። [28]እና
ንተም ከእስራኤላውያን ላይ ከምትቀበሉት

[ሐ]14 የዕብራይስጡ ትርጒም አንድን ነገር ወይም አንድን ሰው በማይለወጥ ውሳኔ ለእግዚአብሔር መስጠትን ያመለክታል።
[T]16 አምሳ አምስት ግራም ያህል ነው።

18፥11 *ለወንድና ለሴት ልጆችህ* ከሚቀርበው ስጦታ ተካፋይ የሚሆኑት ካህናት ብቻ ሳይሆኑ ቤተ ሰቦቻቸውም ጭምር ነበሩ። በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ ያልሆኑ የቤተ ሰብ አባላት ብቻ ሕዝቡ ከሚያመጣው ስጦታና መሥዋዕት እንዳይበሉ ይከለከሉ ነበር (ቍ 13 ይመ)፤ ለመንጻት የሚደረጉ ዝግጅቶች በዘሌ 22፥4-8 ተገልጸዋል።

18፥12 *ምርጥ የወይራ ዘይት... ምርጥ የሆነውን አዲስ የወይን ጠጅና እህል ሁሉ፤* ከተመረተው ሁሉ ምርጥ የሆነውን ለእግዚአብሔር መስጠት የተገባ ነበር፤ ይህም ለካህናትና ለቤተ ሰቦቻቸው የተለየ ምግብ ይሆን ነበር። በተመሳሳይ ሁኔታም በአሁኑ ዘመን የእግዚአብሔርን ቃል በማስተማርና በመስበክ የሚያገለግሉ ሰዎች ለአገልግሎታቸው ተገቢ የሆነ ክፍያ ማግኘት እንዳለባቸው (የ1ቆሮ 9፥3-10 እና ማብ ይመ) የአዲስ ኪዳን ጸሐፊዎች በአጽንዖት ይገልጻሉ።

18፥19 *ዘላለማዊ የጨው ኪዳን፤* በቋሚነት ለካህናት የሚሰጥ ነበር። “የጨው ኪዳን” የሚለው ሐረግ (2ዜና 13፥5 ይመ) አሁንም ግልጽ አይደለም። በዘሌ 2፥13 ከእህል ቍርባን ጋር አብሮ ይቀርብ የነበረው ጨው፣ “የጨው ኪዳን” ተብሎ ተጠርቶአል። በሕዝ 43፥24 እንደ ተጠቀሰው በሚቃጠል መሥዋዕት ላይ ጨው ማድረግ አስፈላጊ ነበር፤ ለቤተ መቅደሱ አገልግሎት ከሚቀመመው ልዩ ዕጣንም ውስጥ ጨው ከተደባለቁት ነገሮች አንዱ ዐይነት እንደ ነበር በዘፀ 30፥35 ተጠቅሶአል። “የጨው ኪዳን” መሥዋዕት ከቀረበ በኋላ በሚበላውና ኪዳን በሚደረግበት ምግብ (ዘፍ 31፥54፤ዘፀ 24፥5-11፤ መዝ 50፥5 ይመ) ላይ የሚጨመረውን ጨው የሚያመለክት ይሆናል። ጨው ለብዙ ጊዜ የሚቆይና ቋሚ የሆነ ነገርን ስለሚወክል፣ የተሰጠውም ኪዳን የማይለወጥ መሆኑን ያመለክታል (ከዘሌ 2፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

*18፥26-32፤* ሌዋውያን፣ ሕዝቡ ለእግዚአብሔር የሚሰጠውን ዐሥራት ተቀብለው ወደ ቤተ መቅደሱ የሚያስገቡ እነርሱ ቢሆኑም ዐሥራትን በመስጠት እግዚአብሔርን የማምለኩ ጕዳይ ራሳቸውንም ይመለከት ነበር። ከሚያገኙት ገቢ አንድ ዐሥረኛውን ለካህኑ ለአሮን መስጠት ይጠበቅባቸው ነበር (ቍ 28)፤ ከሚቀበሉትም የተመረጠው ለእግዚአብሔር መቅረቡን ማረጋገጥ ይገባቸዋል (ቍ 29)። ስለዚህ ሌዋውያን እንደታዘዙት ቢያደርጉ ከሞት ፍርድ ሊያመልጡ ይችላሉ ማለት ነው (ቍ 32)።

ዐሥራት ሁሉ በዚሁ ዐይነት ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መባ ታቀርባላችሁ፤ ከዚሁም የእግዚአብሔር (ያህዌ) ድርሻ የሆነውን ዐሥራት ለካህኑ ለአሮን ትሰጣላችሁ:: [29]ከምትቀበሉት ሁሉ ምርጥና እጅግ የተቀደሰውን ክፍል የእግዚአብሔር (ያህዌ) ድርሻ አድርጋችሁ ታቀርባላችሁ::

[30]"ሌዋውያንን እንዲህ በላቸው፤ 'ምርጥ የሆነውን ክፍል በምታቀርቡበት ጊዜ፣ እንደ ዐውድማ ምርት ወይም እንደ ወይን መጭመቂያ ውጤት ሆኖ ይቈጠርላችኋል:: [31]የቀረው ግን በመገናኛው ድንኳን ለሰጣችሁት አገልግሎት ደመወዛችሁ ስለ ሆነ፣ እናንተና ቤተ ሰዎቻችሁ በየትኛውም ስፍራ ልትበሉት ትችላላችሁ:: [32]የተመረጠውን ክፍል ካቀረባችሁ በዚህ በደለኞች አትሆኑም፤ ደግሞም የተቀደሰውን የእስራኤላውያንን መባ አታረክሱም፤ አትሞቱምም::

## የመንጻት ሥርዐት ውሃ

**19** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [2]"እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘው፣ ሕጉ የሚጠይቀው ሥርዐት ይህ ነው፤ እንከን ወይም ነውር የሌለባትና ቀንበር ተጭኖባት የማያውቅ አንዲት ቀይ ጊደር እንዲያመጡልህ ለእስራኤላውያን ንገራቸው:: [3]ለካህኑ ለአልዓዛርም ስጠው፤ ከሰፈሩ አውጥተውም በፊቱ ይረድዋት:: [4]ከዚያም ካህኑ አልዓዛር ጣቱን በደሙ ውስጥ ነክሮ፣ ወደ መገናኛው ድንኳን ፊት አቅጣጫ ሰባት ጊዜ ይርጨው:: [5]እርሱ እየተመለከተም ጊደሯን ያቃጥሏት፤ ቈዳዋም፣ ሥጋዋም፣ ደሟም፣ ፈርሷም ጭምር ይቃጠል:: [6]ካህኑ የዝግባ ዕንጨት፣ ሂሶጵና ብሩህ ቀይ ክር ወስዶ ጊደሪቱ በምትቃጠልበት እሳት ውስጥ ይጨምር:: [7]ከዚህ በኋላ ካህኑ ልብሱን በውሃ ማጠብ፣ ሰውነቱንም መታጠብ አለበት፤ ከዚያም ወደ ሰፈሩ ሊመለስ ይችላል፤ ይሁን እንጂ በሥርዐቱ መሠረት እስከ ማታ ድረስ የረከሰ ይሆናል:: [8]የሚያቃጥላትም ሰው እንደዚሁ ልብሱን ማጠብ፣ ሰውነቱንም በውሃ መታጠብ አለበት፤ እርሱም ደግሞ እስከ ማታ ድረስ የረከሰ ይሆናል::

18፥28 ሚል3፥8
18፥30 ቍ27
18፥31 ቍ23
18፥32 ቍ29፤ ዘሌ19፥8፤22፥15
19፥2 ዘፍ15፥9፤ ዘሌ22፥19-25፤ዘዳ 21፥3፤1ሳሙ6፥7፤ ዕብ9፥13
19፥3 ዘፀ29፥14፤ ዘኍ3፥4
19፥4 ዘሌ4፥17
19፥5 ዘፀ29፥14
19፥6 ቍ18፤ ዘሌ14፥4፤መዝ51፥7
19፥7 ዘሌ11፥25፤ 14፥8
19፥9 ቍ13፤ዘፍ 35፥2፤ዘፀ29፥31፤ዘሌ 4፥12፤ዘኍ8፥7፤ ዕብ9፥13
19፥10 ዘሌ3፥17፤ 15፥10፤14፥46፤22፥18
19፥11 ዘሌ8፥33፤ 21፥1፤ዘኍ31፥19
19፥12 ቍ19፡20፤ ዘኍ31፥19፤2ዜና 26፥21
19፥13 ቍ22፤ዘሌ 7፥20፤15፥31፤21፥11 ፤22፥3፤2ዜና36፥14፤ መዝ79፥1፤ሕዝ2፥13
19፥15 ዘሌ6፥28
19፥16 ዘኍ31፥19፤ 1ነገ13፥2፤2ነገ23፥6፤ 14፤ሕዝ6፥5፤ማቴ 23፥27፤ዘሌ5፥3
19፥17 ቍ9፤ ዘኍ8፥7
19፥18 ቍ6፡16፤ ዘፀ12፥22፤ዘሌ4፥17

[9]"ንጹሕ የሆነ ሰው የጊደሯን ዐመድ አፍሶ ከሰፈሩ ውጭ በመውሰድ በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ በሆነ ስፍራ ያኑረው፤ ይህም ለመንጻቱ ውሃ እንዲውል በእስራኤል ማኅበረ ሰብ የሚጠበቅ ይሆናል፤ ከኀጢአትም ለመንጻት ይጠቅማል:: [10]የጊደሯን ዐመድ የሚያፈስውም ሰው እንደዚሁ ልብሱን ማጠብ አለበት፤ ያም ሰው እስከ ማታ ድረስ የረከሰ ይሆናል፤ ይህም ለእስራኤላውያን እንዲሁም በመካከላቸው ለሚኖሩ መጻተኞች የሚሆን ዘላለማዊ ሥርዐት ነው::

[11]"የሞተን ሰው በድን የሚነካ ማንኛውም ሰው እስከ ሰባት ቀን የረከሰ ይሆናል:: [12]በሦስተኛውና በሰባተኛውም ቀን ሁለመናውን በውሃው ያንጻ፤ ንጹሕም ይሆናል:: በሦስተኛውና በሰባተኛው ቀን ሁለመናውን ካላነጻ ግን ንጹሕ አይሆንም:: [13]የሞተን ሰው በድን ነክቶ ራሱን ያላነጻ ማንኛውም ሰው የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ማደሪያ ያረክሳል፤ ያም ሰው ከእስራኤል ተለይቶ ይጥፋ:: የሚያነጻው ውሃ ስላልተረጨበት ርኩስ ነው፤ ከርኵሰቱም አልተላቀቀም::

[14]"አንድ ሰው በድንኳን ውስጥ በሚሞትበት ጊዜ የሚፈጸመው ሥርዐት የሚከተለው ነው፤ ወደ ድንኳኑ የሚገባም ሆነ በዚያ ውስጥ ያለ ማንኛውም ሰው እስከ ሰባት ቀን ድረስ የረከሰ ይሆናል፤ [15]እንዲሁም ያልተከደነ ማንኛውም ክፍት ዕቃ የረከሰ ይሆናል::

[16]"ሜዳ ላይ በሰይፍ የተገደለውን ወይም እንዲሁ የሞተውን ወይም ደግሞ ዐፅም ወይም መቃብር የሚነካ ማንኛውም ሰው እስከ ሰባት ቀን ድረስ የረከሰ ይሆናል::

[17]"ለረከሰውም ሰው፣ ለማንጻት ከተቃጠለው የጊደር ዐመድ ላይ ማሰሮ ውስጥ በማድረግ በላዩ የምንጭ ውሃ ይጨምሩበት:: [18]ከዚያም በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ የሆነ ሰው ሂሶጵ ወስዶ በውሃው ውስጥ ከነከረው በኋላ ድንኳኑን፣ በውስጡ ያሉትን ዕቃዎች ሁሉ፣ እዚያ የነበሩትንም ሰዎች ሁሉ ይርጫቸው:: እንዲሁም የሰው ዐፅም ወይም መቃብር ወይም ደግሞ የተገደለውን ወይም እንዲሁ የሞተውን ሰው የነካው ማንኛውንም ሰው ይርጭ:: [19]የነጻው ሰው ያልነጻውን

---

19፥2 *ቀይ ጊደር*፤ በአምልኮ ሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ ያልሆነ ወይም ከመርከሱ የተነሣ በአምልኮ ወደ እግዚአብሔር መቅረብ (ቍ 11፡14፡16) የማይችል ማንኛውም ሰው እንዲነጻ ለማድረግ፣ የቀይ ጊደር መሥዋዕት ይቀርብ ነበር:: ነውር የሌለባት ቀይ ጊደር ከሰፈር ውጭ ታርዳ እንድትቃጠል ይደረጋል (ቍ 3-6):: የተቃጠለውን የጊደሪቱን ዐመድ አፍሶ ከሚያነጻው ውሃ ጋር በመደባለቅ (ቍ 9፡17) የረከሱ ሰዎችን ለማንጻት ይውላል (ቍ 12፡18):: ይህ የረከሱ ሰዎችን የማንጻት ሥርዐት፣ ረክሶ የነበረውን ሰው ተመልሶ ወደ እግዚአብሔር መቅረብ እንዲችል ያደርገዋል:: የዕብራውያን መልእክት፣ የክርስቶስ ደም ያለውን የማንጻት ኀይል ከቀይዋ ጊደር ዐመድ ጋር ያነጻጽረዋል (ዕብ 9፥13-14፤ ቀጥሎም ያለውን ማብ ይመ)::

19፥6 *የዝግባ ዕንጨት፣ ሂሶጵና ብሩህ ቀይ ክር*፤ የቀይዋ ጊደር ዐመድ ካለው የማንጻት ሁኔታ ጋር የተገናኙ ናቸው::

19፥12 *ሁለመናውን በውሃው ያንጻ*፤ የቀይዋ ጊደር ዐመድ ከሰፈር ውጭ ይከማች ነበር፤ የሞተን ሰው በድን የነካ ሰው እንዲነጻ ለማድረግ ዐመዱ በሚፈለገው ሁኔታ ከውሃ ጋር ይደባለቅ ነበር::

19፥13 *የእግዚአብሔርን ማደሪያ ያረክሳል*፤ ከርኵሰቱ እንዲነጻ የተዘጋጀውን መንገድ ሆን ብሎ ችላ የሚል ሰው በራሱ ላይ ፍርድን ማምጣት ብቻ ሳይሆን፣ ለማደሪያው መርከስም ምክንያት ይሆናል:: *ከእስራኤል ተለይቶ ይጥፋ*፤ የዘፀ 12፥15 ማብ ይመ::

19፥14 *ወደ ድንኳኑ የሚገባም ሆነ በዚያ ውስጥ ያለ ማንኛውም ሰው*፤ ሰው የሚረክስባቸው የተለያዩ አጋጣሚዎች ሊኖሩ ይችላሉ፤ የሞተውን ሰው በድን ሆን ብሎ በመንካት ብቻ ሳይሆን፣ በሞተው ሰው በድን አቅራቢያ በመሆን እንኳ ማንኛውም ሰው ሊረክስ ይችላል::

19፥18 *ሂሶጵ ወስዶ በውሃው ውስጥ ከነከረው በኋላ … ይርጫቸው*፤ እዚህ ላይ የመንጻቱ ሥርዐት የሚካሄድበት መንገድ ተገልጾአል:: እንደ ሥርዐቱ ንጹህ የሆነው ሰው፣ ሂሶጵን ወስዶ ንጹሕ ባልሆነው ሰው ወይም ነገር ላይ ይረጭ ነበር:: የክርስቶስ ደም የማንጻት ኀይል፣ የቀይዋ ጊደር ዐመድ የተደባለቀበት ውሃ ርኵሰትን ለማንጻት ካለው ብቃት ጋር ተነጻጽሮአል፤ ("እጅግ አብልጦ" ዕብ 9፥13-14)::

ሰው በሦስተኛውና በሰባተኛው ቀን ይርጨው፤ በሰባተኛው ቀን ያንጻው፤ የሚነጻውም ሰው ልብሱን ይጠብ፤ ገላውንም በውሃ ይታጠብ፤ ማምሻውም ላይ የነጻ ይሆናል። [20]ይሁን እንጂ አንድ የረከሰ ሰው ራሱን ሳያነጻ ከቀረ *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) መቅደስ አርክሶአልና ከማኅበረ ሰቡ ተለይቶ ይጥፋ፤ የሚያነጻው ውሃ ያልተረጨበት ስለ ሆነ ርኩስ ነው። [21]ይህም ለእነርሱ የዘላለም ሥርዐት ነው።

"የሚያነጻውን ውሃ የሚረጨውም ሰው ልብሱን ይጠብ፤ የሚያነጻውንም ውሃ የሚነካ ማንኛውም ሰው እስከ ማምሻው ድረስ የረከሰ ይሆናል። [22]የረከሰ ሰው የሚነካው ማናቸውም ነገር ይረክሳል፤ ይህን የነካ ሰው ደግሞ እስከ ማምሻው ድረስ የረከሰ ይሆናል።"

## ከዐለት የፈለቀ ውሃ

**20** በመጀመሪያው ወር መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ወደ ጺን ምድረ በዳ መጥተው በቃዴስ ተቀመጡ፤ እዚያ ማርያም ሞተች፤ ተቀበረችም።

[2]በዚህ ጊዜ ለማኅበረ ሰቡ የሚሆን ውሃ አልነበረም፤ ሕዝቡም ሙሴንና አሮንን በመቃወም ተሰበሰቡ። [3]ሙሴን ተጣሉት፤ እንዲህም አሉት፤ "ወንድሞቻችን *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት በሞቱ ጊዜ ምነው እኛም ያኔ ሞተን ባረፍነው ኖሮ! [4]*የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ማኅበረ ሰብ ወደዚህ ምድረ በዳ ያመጣችሁት ለምንድነው! ከነከብቶቻችን እዚሁ እንድናልቅ ነውን? [5]ከግብፅ አውጥታችሁ እህል ወይም በለስ፣ ወይን ወይም ሮማን ወደሌለበት ወደዚህ ክፉ ቦታ ያመጣችሁንስ ለምንድነው? የሚጠጣ ውሃ እንኳ ይታጣ!"

[6]ሙሴና አሮን ከማኅበረ ሰቡ ወደ መገናኛው ድንኳን ደጃፍ ሄደው በግንባራቸው ተደፉ፤ *የእግዚአብሔርም* (ያህዌ) ክብር ተገለጠላቸው። [7]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [8]"በትሪቱን ውሰድ፤ አንተና ወንድምህ አሮን ማኅበሩን በአንድነት ሰብስቡ፤ እነርሱም እያዩ ዐለቱን ተናገሩት፤ ዐለቱም ውሃ ያወጣል። አንተም ለማኅበረ ሰቡ ከዐለቱ ውሃ ታወጣላቸዋለህ፤ እነርሱና ከብቶቻቸውም ይጠጣሉ።"

[9]ስለዚህም ሙሴ ልክ እንደታዘዘው በትሩን *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ወሰደ። [10]እርሱና አሮንም ማኅበሩን በዐለቱ ፊት አንድ ላይ ሰበሰቡ፤ ሙሴም፣ "እናንተ ዐመፀኞች አድምጡ፤ ከዚህ ዐለት እኛ ለእናንተ ውሃ ማውጣት አለብን?" አላቸው። [11]ከዚያም ሙሴ እጁን ዘርግቶ በበትሩ ዐለቱን ሁለት ጊዜ መታው፤ ውሃውም ተንዶለዶለ፤ ማኅበረ ሰቡና ከብቶቻቸውም ጠጡ።

[12]ነገር ግን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴንና አሮንን፣ "በእስራኤላውያን ፊት እኔን ቅዱስ አድርጋችሁ ለማክበር ስላልታመናችሁብኝ ይህን ማኅበረ ሰብ ወደምሰጠው ምድር ይዛችሁ አትገቡም" አላቸው።

[13]እስራኤላውያን *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) ጋር የተጣሉበት፣ እርሱም ቅዱስ መሆኑን በመካከላቸው የገለጠበት ይህ የመሪባ[u] ውሃ ነበር።

## ኤዶም እስራኤል እንዳያልፍ ከለከለ

[14]ሙሴ ከቃዴስ ለኤዶም ንጉሥ እንዲህ

[u]13 *መሪባ* ማለት *መጣላት* ማለት ነው።

19፥19 ዘኍ35፥2፤ ዘሌ16፥14-15፤ዘኍ 31፥19፤ሕዝ36፥25፤ ዕብ10፥22
19፥20 ቍ12፤ ዘሌ 14፥8፤15፥31፤ መዝ74፥7
19፥21 ዘፀ27፥21
19፥22 ዘሌ5፥2፤ 15፥4-12
20፥1 ቍ14፤ዘፀ 15፥20፤ዘኍ13፥21፡ 26፤33፥36፤ዘዳ1፥46፤ መሳ11፥17፤መዝ 29፥8
20፥2 ዘፀ15፥22፤ 17፥1፤ዘኍ16፥19
20፥3 ቍ13፤ዘፍ 13፥7፤ዘፀ5፥21፤17፥2፤ 21፥18፤ዘኍ14፥2፤ 16፥31-35
20፥4 ዘፀ14፥11፤ ዘኍ14፥2:3፤16፥13
20፥5 ዘፀ17፥1፤ ዘኍ13፥23፤16፥14
20፥6 ዘፀ40፥2፤ ዘኍ14፥5፤16፥19
20፥8 ዘፀ4፥2፤ 10፥12-13፤17፥6፤ ኢሳ41፥18፤43፥20፤ ኢር31፥9
20፥9 ዘኍ17፥2:10
20፥10 ቍ8፤ መዝ106፥32:33
20፥11 ዘፀ17፥6፤ ኢሳ33፥21
20፥12 ቍ24፤ ዘኍ27፥14፤ዘዳ1፥37፤ 3፥27፤32፥51፤ ኢሳ5፥16፤8፥13
20፥13 ቍ3፤ዘፀ 17፥7፤ዘሌ10፥3
20፥14 ቍ1:16፤ ዘፍ፤24፥3፤25፥30፤

*20፥1-29፤* ይህ ምዕራፍ የማርያምን ሞት (ቍ 1) በማውሳት ይጀምርና በአሮን ሞት ይደመድማል (ቍ 28)። ከኤዶም ጋር የተደረገውንም ግጭት በተመለከተ የተጠቀሰውን ታሪክ ያካትታል (ቍ 14-21)፤ በሙሴ አሳዛኝ ኀጢአትም ላይ ያተኵራል (ቍ 11-12)። በምድረ በዳ የእስራኤል የመጨረሻው ዓመት አሳዛኝ ጅማሬ ይህን የመሰለ ነበር።

20፥1 ***በመጀመሪያው ወር፤*** ዓመቱ አልተጠቀሰም፤ ነገር ግን በቍ 22-29 ያለው ሐሳብ በ33፥38 ላይ ከተገለጸው ጋር ሲነጻጸር ይህ ምዕራፍ የሚጀምረው ከግብፅ ምድር ከወጡ በኋላ በአርባኛው ዓመት ይሆናል ወደሚለው አዝማሚያ ይመራል (የ1፥1፤ 9፥1 ማብ ይመ)። በቃዴስ ዐመፅ በተደረገበት ጊዜ (ም 13፥14) የነበሩ ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ የሆናቸው ብዙ ሰዎች በዚህ ጊዜ ሞተዋል። *በቃዴስ፤* አብዛኛው በምድረ በዳ ያሳለፉት መንከራተት አልተጻፈም፤ ሕዝቦች መና እየበሉ፣ የውሃ ምንጭንና ዘርዘር ብሎ የሚበቅለውን የምድረ በዳ ተክል ለማግኘት የተደጋገመ ጕዞ በማድረግ ብዙ ዞረው ሊሆን ይችላል። ነገር ግን ዞረው የሚመጡት ከፍተኛ ዐመፅ ወደ አደረገበት (ም 13-14) በቃዴስ ወደሚገኘው ዋና ሰፈር ነበር። ዙሪያውን ይዙሩ እንጂ ወደ ተስፋዪቱ ምድር አልደረሱም፤ አሁንም ከፊታቸው ነበረች።

20፥2 ***ውሃ አልነበረም፤*** ከአርባ ዓመት በፊት እግዚአብሔር የዐባይን ወንዝ ለመምታት (ዘፀ 17፥1-7) የተጠቀመበትን በትር እንዲወስድ ሙሴን አዝዞት ነበር። አሁን ደግሞ ከአርባ ዓመት በላይ እስራኤል ከፍተኛ ዐመፅ ባደረጉበት ስፍራ ቀድሞ የሆነው ነገር ተደገመ። የዐመፀኞቹ ልጆች ከሞቱት ዘመዶቻቸው ጋር አብረው ቢሞቱ ይሻላቸው እንደ ነበር ተናገሩ። ከሰማይ የወረደውን መና በሚመለከት ቀድሞ የተሰማው ቅሬታ አሁንም በልጆቻቸው ተደገመ።

20፥8 *ዐለቱን ተናገሩት፤* እግዚአብሔር በግብፅና በዚያ ሁሉ የምድረ በዳ ጕዞ ታምር ያደረገበትን በትር እንዲወስድ ለሙሴ ነግሮት ነበር፤ በዚህ ጊዜ ግን ሙሴ ለሕዝቡ ውሃን ያፈልቅ ዘንድ ዐለቱን መምታት ሳይሆን መናገር ነበረበት (ከመዝ 114፥8 ጋር ያነጻጽሩ)።

20፥10 *እናንተ ዐመፀኞች አድምጡ፤* አርባ ዓመት ሙሉ በሙሴ ልብ ተጠራቅሞ የነበረው ቍጣ፣ ንዴትና ምሬት በአንድ ጊዜ ተገለጠ (መዝ 106፥ 33 ይመ)።

20፥11 *ዐለቱን ሁለት ጊዜ መታው፤* ሙሴ በመቈጣቱ ለድንጋዩ እንዲናገር (ቍ 8) ከእግዚአብሔር የተሰጠውን ትእዛዝ አላከበረም። ሙሴ ተጣድፎ ባለማስተዋል ባደረገው ነገር ከእግዚአብሔር ከባድ ተግሣጽ አደረሰበት (ቍ 12)። ሙሴን ያስቈጣው ነገር ምን እንደ ሆነ በዚህ መጽሐፍ ውስጥ በግልጽ አልተጠቀሰም፤ ይሁን እንጂ ከዚህ ቀጥሎ ያሉት የቍጣው ምክንያቶች ይመስላሉ፤ (1) ቃል ብቻ መናገር በቂ እንዳልሆነ በማሰብ ያደረገው ቢመስልም ሙሴ ይህን የፈጸመው በእግዚአብሔር ካለማመኑ የተነሣ ነበር፤ (2) ህልዎተ እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር እንደ ሆነ የእምነት ቃል ተናግሮ ለሕዝቡ ምላሽ በመስጠት ፈንታ ሙሴ ችኩሎ ባደረገው ነገር (ቍ 12) ቅዱስ የሆነውን እግዚአብሔርን አሳዘነ።

20፥12 ይህን ማኅበረ ሰብ ወደምሰጠው ምድር ይዛችሁ አትገቡም፤ ሙሴ ባለመታዘዙ በመጨረሻ የሚደርስበት ነገር ግልጽ ነው፤ ይኸውም አሮንም ሆነ ሙሴ ወደ ተስፋዪቱ ምድር አለመግባታቸው ነው። አብረዋቸው ከነበሩት መካከል ኢያሱና ካሌብ ብቻ በሕይወት ኖረው ወደ ተስፋዪቱ ምድር ሲገቡ፣ ከሙሴ ጋር አሮንም እንዳይገባ መደረጉ እግዚአብሔርን ባለመቀደሱና ከወንድሙ ጋር በመተባበሩ ነበር።

20፥13 *መሪባ፤* ከአርባ ዓመት በፊት ለመጀመሪያ ጊዜ ከዐለት ውሃ እንዲፈልቅ ሲደረግ ይህንኑ የሚመስል ስም ተጠቅሶ ነበር (በዘፀ 17፥7 ላይ ደግሞ ማሳህ ማለት "መፈተን" ተብሎአል)፤ በመዝ 95፥8 ላይ በመሪባ እና በማሳህ ውሃ አጠገብ የተደረገው ዐመፅ አሳዛኝ መሆኑ በእንጕርጕሮ ተገልጾአል።

*20፥14-21፤* ሙሴ በስምምነት ሕዝቡ ለሚጠቀምበት ነገር ዋጋ ከፍሎ በኤዶም ምድር ያልፍ ዘንድ ላቀረበው ጥያቄ ግትር

ሲል መልእክተኞች ላከ፤

"ወንድምህ እስራኤል የሚለው ይህ ነው፤ የደረሰብን መከራ ሁሉ ምን እንደ ሆነ አንተም ታውቃለህ:: [15]የቀድሞ አባቶቻችን ወደ ግብፅ ወረዱ፤ እኛም እዚያ ብዙ ዘመን ኖርን:: ግብፃውያን እኛንም አባቶቻችንንም አሠቃዩን፤ [16]ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በጮኽን ጊዜ ግን ጩኸታችንን ሰማ፤ መልአክ ልኮም ከግብፅ አወጣን::

"አሁንም ያለነው እዚሁ ቃዴስ በግዛትህ ድንበር ላይ ባለችው ከተማ ነው:: [17]ስለዚህ በአገርህ እንድናልፍ እባክህን ፍቀድልን፤ በየትኛውም ዕርሻ ወይም የወይን ተክል ውስጥ አንገባም፤ ከየትኛውም ጕድጓድ ውሃ አንጠጣም:: የንጉሡን አውራ ጐዳና ይዘን ከመጓዝ በስተቀር፣ ግዛትህን አልፈን እስክንሄድ ድረስ ወደ ቀኝም ወደ ግራም አንልም::"

[18]ኤዶም ግን እንዲህ ሲል መለሰ፤

"በዚህ በኩል አታልፉም፤ እናልፋለን የምትሉ ከሆነ በሰልፍ ወጥተን በሰይፍ እንመታችኋለን::"

[19]እስራኤላውያንም መልሰው፣

"አውራውን መንገድ ይዘን እንሄዳለን፤ እኛም ሆንን ከብቶቻችን የትኛውንም ውሃችሁን ከጠጣን ዋጋውን እንከፍላለን፤ በእግር አልፈን መሄድ ብቻ እንጂ ሌላ ምንም አንፈልግም::" አሏቸው::

[20]ኤዶምም እንደ ገና፣

"በዚህ ማለፍ አትችሉም::" የሚል መልስ ሰጣቸው::

ከዚያም ኤዶም ብዙና ኀይለኛ የሆነ ሰራዊት አሰልፎ ሊወጋቸው ወጣ፤ [21]ስለዚህ ኤዶም በግዛቱ አልፈው እንዳይሄዱ ስለ ከለከላቸው እስራኤላውያን ተመለሱ::

36፥16፤ዘዐ18፥8፤ ዘዳ4፥39፤ኢሱ2፥11፤ 9፥9
20፥15 ዘፍ15፥13፤ 46፥6፤ዘዐ1፥14
20፥16 ቍ14:23፤ ዘፍ16፥11፤21፥17፤ዘዐ 2፥23፤12፥42፤14፥19 ፤ዘኍ33፥37፤ዘዳ26፥8
20፥17 ቍ20፤ ዘኍ21፥22፤ዘዳ2፥27፤ መሳ11፥17
20፥18 ቍ14፤ ዘኍ21፥23
20፥19 ዘዐ12፥38፤ ዘዳ2፥6:28
20፥20 ቍ14: 17:18
20፥21 ዘኍ21፥4: 23፤ዘዳ2፥8፤መሳ11፥18
20፥22 ዘኍ33፥ 37፤34፥7፤ዘዳ1፥46፤ 32፥50
20፥23 ቍ16
20፥24 ቍ10፤ ዘፍ25፥8፤ዘዐ17፥7
20፥25 ዘኍ33፥38
20፥26 ቍ24፤ዘዐ 28፥1-4፤40፥13፤ዘሌ 16፥4፤ዘኍ27፥13፤ 31፥2
20፥27 ዘኍ33፥38
20፥28 ቍ26፤ዘዐ 29፥29፤ዘኍ33፥38፤ ዘዳ10፥6፤32፥50
20፥29 ዘፍ27፥41፤ ዘሌ10፥6፤ዘዳ32፥50፤ 34፥8
21፥1 ዘፍ12፥9፤ ዘኍ 13፥17፤33፥40፤ ዘዳ1፥7፤ኢሱ12፥14፤ መሳ1፥9:16
21፥2 ቍ3፤ዘሌ 7፥16፤ዘዐ22፥20፤ ዘዳ2፥34፤ኢሱ2፥10፤ 8፥26፤ኤር25፥9፤ 50፥21
21፥3 ቍ2፤ዘፍ 10፥18፤ዘኍ14፥45

## የአሮን መሞት

[22]መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ከቃዴስ ተነሥቶ ወደ ሖር ተራራ መጣ:: [23]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) በኤዶም ወሰን አጠገብ ባለው በሖር ተራራ ሙሴንና አሮንን እንዲህ አላቸው፤ [24]"አሮን ወደ ወገኖቹ ይሰበሰባል፤ ሁለታችሁም በመሪባ ውሃ በትእዛዜ ላይ ዐምፃችኋልና ለእስራኤላውያን ወደምሰጣት ምድር አይገባም:: [25]አሮንንና ልጁን አልዓዛርን ወደ ሖር ተራራ ይዘሃቸው ውጣ:: [26]አሮን ወደ ወገኖቹ ስለሚሰበሰብ ልብሱን አውልቀህ ልጁን አልዓዛርን አልብሰው፤ አሮንም እዚያው ይሞታል::"

[27]ሙሴ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዳዘዘው አደረገ፤ መላው ማኅበረ ሰብ እያያቸው ወደ ሖር ተራራ ወጡ:: [28]ሙሴም የአሮንን ልብስ አውልቆ ልጁን አልዓዛርን አለበሰው፤ አሮንም እዚያው ተራራው ጫፍ ላይ ሞተ:: ከዚያም ሙሴና አልዓዛር ከተራራው ወረዱ፤ [29]መላው ማኅበረ ሰብም አሮን መሞቱን በተረዳ ጊዜ፣ የእስራኤል ቤት በሙሉ ሠላሳ ቀን አለቀሰለት::

## የዓራድ መደምሰስ

**21** [1]በኔጌብ ይኖር የነበረው ከነዓናዊው የዓራድ ንጉሥ እስራኤል በአታሪም መንገድ መምጣቱን በሰማ ጊዜ በእስራኤላውያን ላይ አደጋ ጥሎ ጥቂቶቹን ማረከ:: [2]በዚያን ጊዜ እስራኤል፣ "ይህን ሕዝብ አሳልፈህ በእጃችን ከሰጠኸን ከተሞቻቸውን ፈጽሞ እንደመስሳለን"[^] ሲል *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ተሳለ:: [3]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) የእስራኤልን ልመና ሰምቶ ከነዓናውያንን በእጃቸው አሳልፎ ሰጣቸው፤ እነርሱም ሰዎቹንና ከተሞቻቸውን ፈጽመው ደመሰሱ፤ ከዚህ የተነሣም ስፍራው ሖርማ[+] ተባለ::

^2 የዕብራይስጡ ትርጕም አንድን ነገር ወይም አንድን ሕዝብ ፈጽሞ በመደምሰስ፣ በማይሻር ውሳኔ ለእግዚአብሔር መስጠትን ያመለክታል::

+3 መደምሰስ ወይም ማጥፋት ማለት ነው::

የሆነ የእምቢታ መልስ ተሰጠው::

20፥14 *ወንድምህ እስራኤል፤* የኤዶም ሕዝብ የያዕቆብ ወንድም ከሆነው ከዔሳው የትውልድ ሐረግ ነው (ዘፍ 36፥1 ይመ)::

20፥17 *የንጉሡን አውራ ጐዳና፤* በዮርዳኖስ ማዶ የሚገኝና ከአረቢያ እስከ ደማስቆ የሚደርስ ጐዳና ሲሆን፣ የሰሜን ደቡብ ንግድ ዋና መንገድ ነው::

20፥20 *ብዙና ኀይለኛ የሆነ ሰራዊት፤* ኤዶም ሰራዊቱን አሰልፎ በመውጣቱ እስራኤል ወንድሙ ከሆነው ሕዝብ ጋር ጦርነት ላለመግጠም ወደ ኋላ አፈገፈገ:: እስራኤል የጫማ መርገጫ የምታህል መሬት እንኳ ከኤዶም እንዳይወስድ እግዚአብሔር ከልክሎት ነበር (ዘዳ 2፥4-6 ይመ)::

20፥22 *ሖር ተራራ፤* በኤዶም ምድር ዳርቻ እንደሚገኝ (ቍ 23) ከመነገሩ በስተቀር በየት አቅጣጫ እንደ ሆነ የታወቀ ነገር የለም::

20፥24 *ወደ ወገኖቹ ይሰበሰባል፤* በማለዘብ እንደሚሞት የተነገረ አባባል ነው (ዘፍ 25፥8:17፤ 35፥29):: *ሁለታችሁም፤* እግዚአብሔርን ባለመታዘዝ በተደረገው ነገር አሮን ከሙሴ ጋር ተባብሮ ነበር (ቍ 12)፤ በመሆኑም አሮን ሞተ፤ የአሮን ሞት ሙሴም እንደሚሞት የሚያሳይ ቀዳሚ ምልክት ነበር (ዘዳ 34 ይመ)::

20፥25 *አሮንንና ልጁን አልዓዛርን፤* በሙሴ እግር የሚተካው ሰው ማን እንደ ሆነ ግልጽ ነበር (ዘዳ 34)፤ አሮንንም የሚተካው ሰው ማን ሊሆን እንደሚችል የታወቀ ነበር::

*20፥26-28፤* አሮን በሕይወት እያለ ልጁ የእርሱን ልብስ እንዲለብስ ተደረገ፤ አሮን የሞተውም ከዚያ በኋላ ነው::

20፥29 *አለቀሰለት፤* የአሮን (እንዲሁም የሙሴ) ሞት አንድ ትውልድ ማለፉን ያመለክታል:: የቀደመው ትውልድ አሁን ያለፈ ሲሆን በአርባ ዓመት ዕድሜአቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ የሆናቸው ሰዎች ሙሉ በሙሉ ተተክተው ነበር::

*21፥1-3፤* የእስራኤል አዲሱ ማኅበረ ሰብ ከከነዓናውያን ጋር ያደረገው የመጀመሪያው ጦርነት፣ በዓራድ ንጉሥ የተቀሰቀሰ ሳይሆን አይቀርም:: ዓራድ ድንገተኛ ወረራ ሊያደርግባቸው ቢያስብም፣ ድሉ ግን ሙሉ በሙሉ ለእስራኤል ሆነ፤ በቀደመው ትውልድ፣ በአማሌቃውያንና በከነዓናውያን ተሸንፈው ስለ ነበር (14፥41-45)፣ ይህ ለእነርሱ አዲስ ቀን ነበር::

21፥2 *ፈጽሞ እንደመስሳለን፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ::

21፥3 *ሖርማ፤* የዚህን ቦታ ስም መጠቀሱ፣ ቀደም ሲል ከሆነው ከእስራኤል ሽንፈት ጋር የተገናኘ መሆኑን ያረጋግጣል (14፥45 ይመ)::

## ከናስ የተሠራው እባብ

[4]እስራኤላውያን በኤዶም ዞረው ለመሄድ ስላሰቡ ከሖር ተራራ ተነሥተው ወደ ቀይ ባሕር[ᵃ] በሚወስደው መንገድ ተጓዙ፤ ይሁን እንጂ ሕዝቡ በመንገድ ሳለ ትዕግሥቱ አለቀ፤ [5]በእግዚአብሔርና (ኤሎሂም) በሙሴም ላይ ተነሥተው፣ "በምድረ በዳ እንድንሞት ከግብፅ ያወጣችሁን ለምንድነው? ምግብ የለ! ውሃ የለ! ይህን የማይረባ ምግብ ሰውነታችን ተጸይፎታል" ሲሉ ተናገሩ።

[6]በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር (ያህዌ) መርዘኛ እባቦች ሰደደባቸው፤ ሕዝቡን ነደፉ፤ ብዙ እስራኤላውያንም ሞቱ። [7]ሕዝቡም ወደ ሙሴ መጥቶ፣ "በእግዚአብሔርና (ያህዌ) በአንተ ላይ በመናገራችን በድለናል፤ እባቦቹን ከእኛ እንዲያርቅልን ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ) ጸልይልን" አለ፤ ሙሴም ስለ ሕዝቡ ጸለየ።

[8]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "እባብ ሠርተህ በዕንጨት ላይ ስቀለው፤ የተነደፈውም ሁሉ ወደ እርሱ በማየት ይድናል" አለው፤ [9]ስለዚህ ሙሴ የናስ እባብ ሠርቶ በዕንጨት ላይ ሰቀለ፤ ከዚያም በእባብ የተነደፈ ማናቸውም ሰው ወደ ናሱ እባብ በተመለከተ ጊዜ ይድን ነበር።

## ወደ ሞዓብ የተደረገው ጒዞ

[10]እስራኤላውያን ተጓዙ፤ በኦቦትም ሰፈሩ፤ [11]ከዚያም ከኦቦት ተነሥተው፣ በፀሓይ መውጫ ትይዩ ባለው ምድረ በዳ በዒዮዓባሪም ሰፈሩ። [12]ከዚያም ተጒዘው በዘሬድ ሸለቆ ሰፈሩ። [13]ከዚያም ተነሥተው እስከ አሞራውያን ግዛት በሚዘልቀው ምድረ በዳ ባለው በአርኖን አጠገብ ሰፈሩ፤ አርኖን በሞዓብና በአሞራውያን መካከል የሚገኝ የሞዓብ ወሰን ነው። [14]እንግዲህ በእግዚአብሔር (ያህዌ) የጦርነት መጽሐፍ እንዲህ ተብሎ የተጻፈው በዚሁ የተነሣ ነው፤

"…በሱፋ[ᵇ] ውስጥ የሚገኘው ዋሄብ አርኖንና [15]ወደ ዔር የሚወስዱት በሞዓብ ድንበርም የሚገኙት የሸለቆች ተረተሮች።"

[16]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ፣ "ሰዎቹን በአንድነት ሰብስባቸውና ውሃ እሰጣቸዋለሁ" ወዳለበት ብኤር ወደተባለው የውሃ ጒድጓድ ጒዞአቸውን ቀጠሉ።

[17]ከዚያም እስራኤል ይህን መዝሙር ዘመረ፤

"አንተ ምንጭ ሆይ ፍለቅ!
እናንተም ዘምሩለት፤
[18]ልዑላን ለቈፈሩት፣
የሕዝብ አለቆች በበትረ
መንግሥታቸውና በበትሮቻቸው
ላጐደጐዱት፣
የውሃ ጒድጓድ ዘምሩለት።"

ከዚህ በኋላ ከምድረ በዳው ወደ መቴና ሄዱ፤ [19]ከመቴና ወደ ነሃሊኤል፣ ከነሃሊኤልም ወደ ባሞት፣ [20]ከባሞትም ፊስጋ ላይ ሆኖ ምድረ በዳው ቊልቊል ወደሚታይበት በሞዓብ ወደሚገኘው ሸለቆ ተጓዙ።

## የሴዎንና የዐግ ድል መሆን

[21]እስራኤል ወደ አሞራውያን ንጉሥ ወደ ሴዎን እንዲህ የሚሉ መልእክተኞች ላከ፤

[22]"በአገርህ አልፈን እንድንሄድ ፍቀድልን፤ ወደ የትኛውም ዕርሻ ሆነ የወይን አትክልት አንገባም፤ ወይም ከየትኛውም ጒድጓድ ውሃ አንጠጣም። ከግዛትህ እስክንወጣ ድረስም የንጉሡን አውራ ጐዳና አንለቅም።"

[23]ሴዎን ግን እስራኤል በግዛቱ ውስጥ እንዲያልፍ አልፈቀደም፤ ሰራዊቱን በሙሉ አሰባስቦ እስራኤልን ለመውጋት ወደ ምድረ

ᵃ4 በዕብራይስጥ ያም ሱፍ ሲሆን፣ የደንገል ባሕር ማለት ነው።
ᵇ14 የዕብራይስጡ ትርጒም አይታወቅም።

21፥4 ዘኍ14፥25፤ 20፥21:22፤ዘዳ2፥1:8፤ 11፥14፤መሳ11፥18
21፥5 ዘፀ14፥11፤ ዘኍ11፥5:20፤14፥2:3 ፤20፥5፤መዝ78፥19
21፥6 ቊ7፤ዘዳ8፥ 15፤32፥33፤ኢዮ20፥ 14፤መዝ58፥4፤140፥3 ፤ኤር8፥17፤1ቆሮ10፥9
21፥7 ዘፀ8፥8፤ዘኍ 11፥2፤14፥40፤1ሳሙ 7፥8፤መዝ78፥34፤ኤር 27፥18፤37፥3፤ሆሴ 5፥15፤ሐሥ8፥24
21፥8 ዮሐ3፥14
21፥9 2ነገ18፥4፤ ዮሐ3፥14-15
21፥10 ዘኍ33፥43
21፥11 ዘፍ36፥35፤ ዘኍ33፥44፤ዘዳ34፥8፤ ኤር40፥11
21፥12 ዘዳ2፥13:14
21፥13 ዘፍ10፥16፤ ዘኍ22፥36፤ዘዳ2፥24፤ ኢሱ12፥1፤መሳ11፥13 :18፤2ነገ10፥33፤ኢሳ 16፥2፤ኤር48፥20
21፥14 1ሳሙ17፥ 47፤18፥17፤25፥28
21፥15 ቊ28፤ዘዳ 2፥9:18፤ኢሳ15፥1
21፥16 ዘኍ25፥1፤ 33፥49፤መሳ9፥21፤ ኢሳ15፥8
21፥17 ዘፀ15፥1
21፥20 ዘኍ23፥14፤ ዘዳ3፥17:27፤34፥1፤ ኢሱ12፥3፤13፥20
21፥21 ዘፍ32፥3፤ ዘፀ23፥23፤ዘኍ32፥ 33፤ዘዳ1፥4፤ኢሱ2፥ 10፤12፥2:4፤13፥10፤ መሳ11፥19-21፤1ነገ 4፥19፤ነህ9፥22፤መዝ 135፥11፤136፥19፤ ኤር48፥45
21፥22 ዘኍ20፥17
21፥23 ዘኍ20፥18: 21፤ዘዳ2፥32፤ኢሱ13፥ 18፤21፥36፤መሳ11፥ 20፤ኢሳ15፥4፤ኤር 48፥21:34

---

*21፥4፤* ሙሴ ከኤዶም ጋር ጦርነት ላለመግጠም በመወሰኑ (የ20፥20 ማብ ይመ) ሕዝቦች በእግዚአብሔር ምሪትና በሙሴ ላይ በቍጣ ተናገሩ። ብዙ ድል በማግኘታቸውም በራሳቸው ተማምነው ነበር። በዓራድ ንጉሥ ላይ ያገኙት ድል ለተሳሉት ስእለት ምላሽ ለመስጠት (ቍ 2) በእግዚአብሔር የተደረገ መሆኑን ዘነጉት፤ አሁንም በእግዚአብሔር ላይ ለማመፅ ተዘጋጅተው ነበር።

21፥5 *ይህን የማይረባ ምግብ ሰውነታችን ተጸይፎታል፤* ሕዝቡ ትዕግሥት ከማጣቱ የተነሣ (ቍ 4) የእግዚአብሔርን ክብር ለማቃለል፣ የእርሱ አገልጋይ የሆነውን ሙሴን ለመናቅና ከሰማይ የወረደውን መና ለመጸየፍ ተዳፈረ። ስለ መናው ሕዝቡ ከተናገረው የነቀፋ ቃል ሁሉ ይኸኛው እጅግ የከፋ ነው (የ11፥7 ማብ ይመ)። ሙሴ ድንጋዩን በቍጣ መምታቱ ሊሆን ከሚገባው ግምት ውጪ (የ20፥11 ማብ ይመ) እንደ ሆኑ ሁሉ፣ ሕዝቡ ከሰማይ ለወረደው እንጀራ ያሳየው ንቀትና መጸየፍ እጅግ የከፋ ነበር። ከሰማይ የወረደውን እንጀራ መናቅ የእግዚአብሔርን ክብር ከማቃለል ተለይቶ የሚታይ አይደለም (ከዮሐ 6፥32-35፡ 48-51:58 ጋር ያነጻጽሩ)።

*21፥8-9፤* ሕዝቡ በኀጢአታቸው ተጸጽተው ላደረጉት ጸሎት ምላሽ ይሆን ዘንድ (ቍ 7) በእባብ የተነደፈም ሁሉ አይቶ እንዲድን የእባብ ምስል ሠርቶ ቋዐላማ ወይም በዕንጨት ላይ እንዲሰቅል እግዚአብሔር ሙሴን አዘዘው። የዚህን ድርጊት ምሳሌያዊ አገላለጽ በዮሐ 3፥14-15 ይመ።

*21፥10-13፤* ሕዝቡ በኤዶም ዳርቻ አድርገው፣ በስተ ምዕራብ ወደ ጨው ባሕር ማዕከላዊ ክፍል ወደሚገባው፣ በሞአብና በአሞራውያን ግዛት መካከል አዋሳኝ ወደ ሆነው ወደ አርኖን ወንዝ አመራ።

21፥14 *በእግዚአብሔር የጦርነት መጽሐፍ፤* በብሉይ ኪዳን ውስጥ የተጠቀሰው እዚህ ቦታ ብቻ ነው። እግዚአብሔርን የሚያወድሱ የተለያዩ ጥንታዊ የጦርነት መዝሙሮችን የያዘ መጽሐፍ ሊሆን ይችላል (ስለ ጦርነት ጊዜ ሙዚቃ ለመረዳት የ10፥3 ማብ ይመ)። ከ"ያሻር መጽሐፍ" ጋር ያነጻጽሩ (ኢሱ 10፥13፤ 2ሳሙ 1፥18)።

21፥16 *ውሃ እሰጣቸዋለሁ፤* በምድረ በዳው ጒዞ ወቅት ውሃን በተመለከተ የሚነሣው ጥያቄ የተደጋገሙ ችግሮች ተከሥተው ነበር (ም 20፤ ዘፀ 17 ይመ)።

*21፥17-18፤* የውሃው ምንጭ መዝሙርም የተገኘው ከእግዚአብሔር የጦርነት መጽሐፍ (ቍ 14) ሊሆን ይችላል።

*21፥21-26፤* እስራኤል የኤዶምን ንጉሥ እንደ ጠየቀ ሁሉ (20፥14-19) በአሞራውያንም ምድር ማለፍ ይችሉ ዘንድ የአሞራውያንን ንጉሥ ጠየቀ። ሴዎን ኀይሉን አሰልፎ እስራኤልን ሊገጥም በሞከረ ጊዜ ድል ተመታ። የአሞራውያን የነበረው ምድር የሚገኘው ከዮርዳኖስ ማዶ ሲሆን፣ ከአርኖን ወንዝ (የጨው ባሕር አማካይ) ጀምሮ ከጨው ባሕር በስተ ሰሜን ሠላሳ ስምንት ኪሎ ሜትር ያህል ርቆ ወደሚገኘው ዮርዳኖስ ወንዝ ወደሚፈሰው ያቦቅ ወንዝ (ቍ 24) ድረስ ነው።

በዳው ወጣ፤ ያህጽ እንደ ደረሰም ከእስራኤል ጋር ጦርነት ገጠመ:: [24]እስራኤል ግን በሰይፍ መታው፤ ከአርኖን እስከ ያቦቅ ድረስ ያለውንም ምድሩን ወሰደበት፤ ይሁን እንጂ የአሞናውያን ወሰን የተመሸገ ስለ ነበር ከያቦቅ አላለፈም:: [25]እስራኤልም ሐሴቦንና በአካባቢዋ ያሉትን መንደሮች ጨምሮ የአሞራውያንን ከተሞች በሙሉ በመያዝ እዚያው ተቀመጠ:: [26]ሐሴቦን የቀድሞውን የሞዓብን ንጉሥ ወግቶ እስከ አርኖን ድረስ ያለውን ምድሩን የወሰደበት የአሞራውያን ንጉሥ የሴዎን ከተማ ነበረች::

[27]እንግዲህ ባለቅኔዎች እንደዚህ ያሉት ለዚህ ነው፤

"ወደ ሐሴቦን ኑ፣ እንደ ገና ትገንባ፤
የሴዎንም ከተማ ተመልሳ ትሠራ፤

[28]"እሳት ከሐሴቦን ወጣ፤
ነበልባልም ከሴዎን ከተማ ተንቦገቦገ፤
የሞዓብን ዔር፣
በአርኖን ከፍታዎች የሚኖሩትንም በላ::
[29]ሞዓብ ሆይ፤ ወዮልህ!
የከሞስ ሕዝብ ሆይ፤ ተደመሰስህ!
ወንዶች ልጆቹን ለሽሽት፣
ሴቶች ልጆቹን ለምርኮ፣
ለአሞራውያን ንጉሥ ለሴዎን አሳልፎ ሰጥቶአል::

[30]"እኛ ግን ገለበጥናቸው፤
ሐሴቦን እስከ ዴቦን ድረስ ተደመሰሰች፤
እስከ ኖፋ ድረስ ያሉትን፣
እስከ ሜድባ የተዘረጉትን
እንዳሉ አፈራርሰናቸዋል::"

[31]ስለዚህም እስራኤል በአሞራውያን ምድር ተቀመጠ::

[32]ሙሴ ሰላዮችን ወደ ኢያዜር ከላከ በኋላ እስራኤላውያን በአካባቢዋ ያሉትን መንደሮች በመያዝ እዚያ የነበሩትን አሞራውያን አባረሩአቸው:: [33]ከዚያም ተመልሰው ወደ ባሳን የሚወስደውን መንገድ በመያዝ ሄዱ፤ የባሳን ንጉሥ ዐግና መላ ሰራዊቱም ኤድራይ ላይ ጦርነት ሊገጥማቸው ወጡ::

[34]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "እርሱን ከመላው ሰራዊቱና ከምድሩ ጋር በእጅህ አሳልፌ ሰጥቼሃለሁና አትፍራው:: በሐሴቦን ሆኖ ይገዛ በነበረው በአሞራውያን ንጉሥ በሴዎን ላይ ያደረግህበትን ሁሉ በእርሱም ላይ አድርግበት" አለው::

[35]ስለዚህም እስራኤላውያን ዐግን ከልጆቹና ከመላው ሰራዊቱ ጋር አንድም ሳይቀሩ ሁሉንም ፈጇቸው፤ ምድሩንም ወረሱ::

### ባላቅ በለዓምን አስጠራ

**22** ከዚህ በኋላ እስራኤላውያን ወደ ሞዓብ ሜዳ ተጕዘው ከዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ ከኢያሪኮ[a] ማዶ ሰፈሩ::

[2]በዚህ ጊዜ የሴፎር ልጅ ባላቅ፣ እስራኤል በአሞራውያን ላይ ያደረገውን ሁሉ አየ፤ [3]ሞዓብም ከሕዝቡ ብዛት የተነሣ ተሸበረ፤ በእርግጥም ሞዓብ በእስራኤላውያን ምክንያት በፍርሀት ተውጦ ነበር::

[4]ሞዓባውያንም የምድያምን ሽማግሌዎች፣ "በሬ የመስክ ሣር ጠራርጎ እንደሚበላ ሁሉ፣ ይህም ሰራዊት በዙሪያችን ያለውን ሁሉ ጠራርጎ የሚያጠፋ ነው" አሏቸው::

ስለዚህ በዚያን ጊዜ የሞዓብ ንጉሥ የነበረው የሴፎር ልጅ ባላቅ፣ [5]ከወንዙ[b] ዳር ባለች በትውልድ አገሩ በምትገኝ በፋቱራ የነበረውን የቢዖርን ልጅ በለዓምን እንዲጠሩት መልእክተኞች ላከ፤ እንዲህም አለ፤

> እነሆ ከብዛቱ የተነሣ ምድሩን የሸፈነ ሕዝብ ከግብፅ ወጥቶ በአቅራቢያዬ ሰፍሮአል:: [6]ስለዚህ ይህን ሕዝብ መቋቋም ስለማልችል መጥተህ ርገምልኝ፤ ምናልባትም ድል አድርጌ ከአገሬ ላስወጣቸው የምችለው ከዚያ በኋላ ሊሆን ይችላል፤ አንተ የምትባርከው ቡሩክ፣ የምትረግመውም ርጉም እንደሚሆን ዐውቃለሁና::"

[7]የሞዓብና የምድያም ሽማግሌዎችም ለሟርት የሚከፈለውን ዋጋ ይዘው ሄዱ፤ በለዓም ዘንድ በደረሱ ጊዜም የባላቅን መልእክት ነገሩት::

21፥24 ቍ35፤ዘፍ 19፥38፤32፥22፤ዘኍ 32፥33፤ዘዳ2፥33፡37፤ 3፥3፡4፤29፥7፤ኢሱ13፥ 10፤መሳ2፥37፤11፥13 ፡22፤መዝ፤135፥ 10-11አሞ2፥9
21፥25 ቍ30፤ዘኍ 13፥29፤32፥3፤ዘዳ1፥4 ፤29፥7፤ኢሱ9፥10፤ 12፥2መሳ10፥11፤11፥ 26ኢሳ15፥4፤16፥8፤ ኤር48፥2፡34፤አሞ 2፥10
21፥26 ቍ11፡13፤ 21፤ዘኍ13፥29፤ዘዳ 29፥7፤መዝ135፥11
21፥28 ቍ15፤ዘኍ 11፥1፤22፥41፤ዘዳ 12፥2፣ኢሱ13፥17፤ ኢሳ15፥2፤ኤር19፥5፤ 48፥45
21፥29 ዘኍ24፥17፤ መሳ10፥6፤11፥24፤ ሩት1፥15፤2ሳሙ8፥2፤ መዝ60፥8፤1ነገ11፥7፡ 33፤2ነገ፤23፥13፤1ዜና 18፥2፤ኢሳ15፥5፤16፥2 ፤25፥10ኤር48፥7፡46
21፥30 ዘኍ32፥3፤ ኢሱ13፥9፡16፡17፤ ነህ11፥25፤1ዜና19፥7 ኢሳ15፥2፤ኤር 48፥18፡22፤
21፥31 ዘኍ13፥29
21፥32 ዘኍ32፥1፡ 3፡35፤ኢሱ2፥1፤6፥22፤ 7፥2፤ኢሱ13፥25፤መሳ 18፥2፤2ሳሙ10፥3፤ 2ሳሙ24፥5፤1ዜና19፥ 3፤1ዜና6፥81፤ኢሳ 16፥8፤ኤር48፥32
21፥33 ዘኍ32፥33፤ ዘዳ1፥4፤3፥1፡3፡4፡10፥ 31፥4፤32፥14፤ኢሱ2፥ 10፤9፥10፤12፥4፤13፥ 12፡30፡31፤19፥37፤ 1ነገ4፥13፡19፤ነህ9፥ 22፤መዝ135፥11፤ 136፥20
21፥34 ዘዳ3፥2
21፥35 ቍ24ኢሱ 9፥10
22፥1 ዘኍ13፥29፤ 21፥11፤31፥12፤33፥ 48፤ዘዳ32፥49፤ኢሱ 2፥1፡7
22፥2 ዘኍ23፥1-3፤ ኢሱ24፥9፤መሳ11፥25 ፤ሚክ6፥5፤ራእ2፥14
22፥3 ዘፀ15፥15
22፥4 ዘፍ19፥37፤ 25፥2፤ዘኍ32፥17፡18፡29፤ኢዮ5፥25፤መዝ72፥16 22፥5 ቍ7፤ዘፍ 2፥14፤ዘፀ13፥3ዘኍ24፥25፤31፥8፡16፤ዘዳ23፥4፤ኢሱ13፥22፤ነህ 13፥2፤ሚክ6፥5፤2ጴጥ2፥15 22፥6 ቍ11፡12፡17፤ዘኍ23፥7፡ 11፡13፤24፥9፡10 22፥7 ዘፍ30፥27

[a]1 በዕብራይስጥ *የኢያሪኮ ዮርዳኖስ* የሚባል ሲሆን፣ ይህም የዮርዳኖስ ወንዝ የጥንት ስም ሳይሆን አይቀርም::
[b]5 የኤፍራጥስ ወንዝ ነው::

*21፥27-30፤* በዚህ ምዕራፍ ላይ የሚገኘው ይህ ሦስተኛው ጥንታዊ ግጥም፣ አሞራውያን በሞዓብ ላይ ስለ አገኙት ድል (ቍ 29) የተዘመረና ተሸናፊውን ወገን የሚያስቈጣ የአሞራውያን መዝሙር ነበር:: "የሐሴቦን መዝሙር" ደግሞ በእግዚአብሔር የጦርነት መጽሐፍ ተጽፎ እንዲቈይ ተደርጐ ይሆናል (ቍ 14)::

21፥33 *ባሳን፤* ከገሊላ ባሕር በስተ ሰሜን ምሥራቅ የሚገኝ አገር ነው::

21፥35 *ሁሉንም ፈጇቸው፤* እስራኤላውያን ግን ካሸነፉት በኋላ ከዮርዳኖስ ማዶ ያለውን አገር፣ ይኸውም ከሞአብ ጀምሮ በሔርሞን ተራራ አካባቢ የሚገኙት እስከ ባሳን ከፍታዎች ድረስ ያሉትን አገሮች ተቈጣጠሩ:: በሴዎንና በዖግ ላይ የተገኘውን ድል ለማብሰር መዝሙር ተዘምሮአል፤ (መዝ 135፥11፤ 136፥19-20)፤ እግዚአብሔር ላደረገውም ነገር መታሰቢያ በሚከበርበት በፋሲካ በዓል ዕለት በቋሚነት ከሚጠቀሱት ነገሮች አንዱ ነው::

22፥1 *ሞዓብ ሜዳ፤* የእስራኤል ሕዝብ ከጨው ባሕር በስተ ሰሜን፣ ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተ ምሥራቅ ወዳለው የሰፈራ ቦታቸው ተመልሶ ሄደ:: ከጥንታዊዋ የኢያሪኮ ከተማ በመጀመር በከነዓን ላይ ጦርነት የከፈቱት ከዚህ ቦታ ተነሥተው ነበር:: ነገር ግን ሞዓብ የእስራኤል ዕቅድና ሁኔታ አላስተማመነውም:: የሞዓብ ፍራት በእስራኤል የመውረስ ታሪክ ሂደት ውስጥ ክፍተት በመፍጠር ታሪክ እንዲቋረጥ ያደርጋል፤ በክፍተቱ መኻል የሚታየው የባላቅና የበለዓም ታሪክ ነው (ም 22-24)::

22፥3 *ሞዓብ... በፍርሀት ተውጦ ነበር፤* የሞዓብ ንጉሥ ባላቅ፣ እስራኤል በእርሱ ላይ ያቀዱት ክፉ ነገር እንደ ሌለ አላወቀም ነበር::

22፥4 *የምድያምን ሽማግሌዎች ... አሉአቸው፤* እስራኤልን ለመቃወም (ቍ 7) ባላቅ ከምድያማውያን ጋር ኅብረት ፈጠረ:: *በሬ የመስክ ሣር ጠራርጎ እንደሚበላ፤* የሚለው አባባል ሕዝቦች ከብት አርቢዎች መሆናቸውን ለማመልከት የገባ ምሳሌያዊ ንጽጽር ነው::

*22፥5 የቢዖርን ልጅ በለዓምን እንዲጠሩት፤* ባላቅ ወታደር አሰልፎ እስራኤልን ለመዋጋትና ለመቋቋም እንደማይቻል ስለ ተረዳ፣ ወደ ፊት የሚሆነውን ነገር በመተንበይና በመርገም

[8]በለዓምም፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚሰጠኝን መልስ አመጣላችኋለሁና የዛሬን ሌሊት እዚሁ ዕደሩ" አላቸው። ስለዚህም የሞዓብ አለቆች ከእርሱ ዘንድ ቈዩ።

[9]እግዚአብሔርም (ኤሎሂም) ወደ በለዓም መጥቶ፣ "ከአንተ ጋር ያሉት እነዚህ ሰዎች እነማን ናቸው?" ሲል ጠየቀው።

[10]በለዓምም እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) እንዲህ አለው፤ "የሞዓብ ንጉሥ የሴፎር ልጅ ባላቅ ይህን መልእክት ልኮብኛል፤ [11]'ከግብፅ የወጣ ሕዝብ የምድሩን ገጽ አጥለቅልቆታል፤ ስለዚህ መጥተህ ርገምልኝ፤ ምናልባት ልዋጋቸውና ላባርራቸው የምችለው ከዚያ በኋላ ሊሆን ይችላል።' "

[12]እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ግን በለዓምን፣ "አብረሃቸው አትሂድ፤ የተባረከ ሕዝብ ስለ ሆነም አትርገመው" አለው።

[13]በማግሥቱ ጠዋት በለዓም ተነሥቶ የባላቅን አለቆች፣ "አብሬአችሁ እንዳልሄድ እግዚአብሔር (ያህዌ) ከልክሎኛልና እናንተ ወደ አገራችሁ ተመለሱ አላቸው።"

[14]ስለዚህ የሞዓብ አለቆች ወደ ባላቅ ተመልሰው፣ "በለዓም አብሮን ለመምጣት እምቢ አለን" አሉት።

[15]ከዚያም ባላቅ ከፊተኞቹ ይልቅ ቍጥራቸው የበዛና ይበልጥ የተከበሩ ሌሎች አለቆች ላከ። [16]እነርሱም ወደ በለዓም መጥተው እንዲህ አሉት፤ "የሴፎር ልጅ ባላቅ ይህን እንድንነግርህ ልኮናል፤ ወደ እኔ ለመምጣት የሚያግድህ ምንም ነገር አይኑር፤ [17]ወሮታህን በእጅጉ እከፍላለሁ፤ የምትለውንም ሁሉ አደርጋለሁ፤ ስለዚህ መጥተህ ይህን ሕዝብ ርገምልኝ።"

[18]በለዓም ግን እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "ሌላው ይቅርና ባላቅ በብርና በወርቅ የተሞላ ቤተ መንግሥቱን ቢሰጠኝ እንኳ፣ የአምላኬን የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም ያህዌ) ትእዛዝ በመጣስ ከዚያ ያለፈ ወይም ያነሰ ማንኛውንም ነገር ማድረግ አልችልም። [19]አሁንም ሌሎቹ እንዳደረጉት ሁሉ፣ እናንተም ዛሬ እዚሁ ዕደሩና እግዚአብሔር (ያህዌ) ምን እንደሚለኝ ደግሞ ልወቅ።"

[20]በዚያች ሌሊት እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ወደ በለዓም መጥቶ፣ "እነዚህ ሰዎች የመጡት እንድትሄድላቸው እስከ ሆነ ድረስ አብረሃቸው ሂድ፤ ነገር ግን እኔ የምነግርህን ብቻ አድርግ።"

## የበለዓም አህያ

[21]በለዓም በጠዋት ተነሣ፤ አህያውንም ጭኖ ከሞዓብ አለቆች ጋር ሄደ። [22]ይሁን እንጂ በለዓም በሄደ ጊዜ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) በጣም ተቈጥቶ ስለ ነበር የእግዚአብሔር (ያህዌ) መልአክ ሊቃወመው በመንገዱ ላይ ቆመ። በለዓምም በአህያው ላይ ተቀምጦ ነበር፤ ሁለት አሽከሮቹም አብረው ነበሩ። [23]አህያዪቱም የእግዚአብሔር (ያህዌ) መልአክ የተመዘዘ ሰይፍ ይዞ በመንገድ ላይ መቆሙን ባየች ጊዜ ከመንገድ ወጥታ ዕርሻ ውስጥ ገባች፤ በለዓምም ወደ መንገዱ እንድትመለስ መታት።

[24]ከዚያም የእግዚአብሔር (ያህዌ) መልአክ በሁለቱም በኩል ግንብ ባለበት በሁለት የወይን ተክል ቦታ መካከል በሚገኝ ጠባብ መተላለፊያ ላይ ቆመ። [25]አህያዪቱም የእግዚአብሔርን (ያህዌ) መልአክ ባየች ጊዜ ወደ ግንቡ ተጠግታ የበለዓምን እግር አጣበቀችው፤ ስለዚህም እንደ ገና መታት።

[26]የእግዚአብሔርም (ያህዌ) መልአክ ወደ ፊት ሄድ ብሎ ወደ ቀኝም ሆነ ወደ ግራ መተላለፊያ በሌለበት ጠባብ ቦታ ላይ ቆመ። [27]አህያዪቱም የእግዚአብሔርን (ያህዌ) መልአክ ባየች ጊዜ ከበለዓም በታች ተኛች፤ በለዓም ተቈጥቶ ነበርና በበትሩ ደበደባት። [28]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) የአህያዪቱን አፍ ከፈተ፤ በለዓምንም፣ "እንዲህ አድርገህ ሦስት ጊዜ የመታኸኝ ምን አድርጌህ ነው?" አለችው።

22፥8 ቍ 19
22፥9 ቍ 20፤ ዘፍ 20፥3፤ ዘኍ 23፥5፤ 24፥4፡16
22፥12 ዘፍ 12፥2
22፥17 ቍ 6፡37፤ ዘኍ 24፥11
22፥18 ቍ 38፤ ዘኍ 23፥12፡26፤ 24፥13፤ 1ነገ 22፥14፤ 2ዜና 18፥13፤ ኤር 42፥4፤
22፥19 ቍ 8
22፥20 ቍ 35፡38፤ ዘፍ 20፥3፤ ዘኍ 23፥5፡12፡16፡26፤ 24፥13፤ 2ዜና 18፥13
22፥22 ዘፍ 16፥7፤ ዘፀ 4፥14፤ መሳ 13፥3፡6፡13
22፥23 ቍ 25፡27፤ ኢያ 5፥13
22፥27 ዘኍ 11፥1፤ ያዕ 1፥19
22፥28 ቍ 32፤ 2ጴጥ 2፥16

ታዋቂ የሆነውን ሰው በማስጠራት በጣዖት አምላኪዎች የሟሟረት አሠራር (ቍ 6-7) እስራኤልን ለማስረገም ፈለገ።

22፥8 ***እግዚአብሔር የሚሰጠኝን መልስ፤*** እዚህ ላይ ያለውን ሐረግና በቍ 18 ላይ፣ "አምላኬ እግዚአብሔር" የሚለውን በማየት አንዳንዶች በለዓም በእስራኤል አምላክ "በያህዌ" የሚያምን ሰው ነበር እስከ ማለት ደርሰዋል። ነገር ግን ተከታዩን አገላለጽ መሠረት በማድረግ በለዓም የተናገረው ነገር ራሱን የማንኛውም አማልክት ቃል አቀባይ መሆኑን የሚገልጽ አድርጎ መውሰዱ ይበልጥ ተቀባይነት ያለው ይመስላል፤ (31፥7-8፡ 15-16፣ ዘዳ 23፥3-6፤ ኢያ 13፥22፤ 24፥9-10፤ ነህ 13፥1-3፤ ሚክ 6፥5፤ 2ጴጥ 2፥15-16፣ ይሁ ቍ 11፤ ራእ 2፥14 ይመ)።

22፥9 ***እግዚአብሔርም ወደ በለዓም መጥቶ፤*** በለዓም "ያህዌ" (ቍ 8) ብሎ በተናገረው ቃል ፈንታ፣ "አምላክ" ብሎ በመጻፍ፣ ጸሐፊው ለባዕድ አማልክት ነቢይ ለሆነው በለዓም ያለውን ጥላቻ ያመለክታል። በለዓም ራሱን ትክክለኛ የእግዚአብሔር ነቢይ አድርጎ በመቍጠር ከተናገረው የሚያስቈጣ ቃል አንጻር ብልኀት በሞላበት ዘዴ ተራኪው ራሱን ያርቃል። እግዚአብሔር በለዓምን መናገሩ የማይካድ ነው፤ የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር ግን ከሌሎች አማልክት የተለየ መሆኑን በለዓም ገና አልተረዳም ነበር።

22፥12 ***የተባረከ፤*** ለአብርሃም በተሰጠው ተስፋ መሠረት እስራኤል በእግዚአብሔር በረከት ሥር ነበር (ዘፍ 12፥2-3)።

22፥18 ***የአምላኬን የእግዚአብሔርን፤*** በለዓም፣ "የአምላኬን የእግዚአብሔርን" ብሎ መናገሩ ከሚያመልካቸው ብዙ አማልክት መካከል የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔርንም የሚያካትት መሆኑን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል። መጽሐፍ ቅዱስ፣ በለዓምን ጽድቅ ከመፈለግ ይልቅ በገንዘብ ጥቅም የሚደለል ሰው ምሳሌ አድርጎ ይገልጸዋል (ዘዳ 23፥3-6፤ 2ጴጥ 2፥15-16፤ ይሁ ቍ 11)።

22፥20 ***አብረሃቸው ሂድ፤*** ቀደም ሲል በለዓም እንዳይሄድ መከልከሉና (ቍ 12) በጕዞ ላይ እያለ በእርሱ ላይ መቈጣቱ (ቍ 22)፣ እዚህ ላይ ደግሞ በለዓም እንዲሄድ እግዚአብሔር መፍቀዱ፣ እርስ በእርሱ የሚቃረን ሐሳብ ይመስላል። ችግሩ ግን የበለዓም ወላዋይ ባሕርይ እንደ ሆነ ግልጽ ነው። እስራኤልን ለመርገም እንዳይሄድ እግዚአብሔር በለዓምን ከልክሎታል፤ ቀጥሎም ትእዛዙን የሚያከብር ከሆነ ብቻ እንዲሄድ ፈቅዶለታል። እግዚአብሔር ግን የበለዓምን ድብቅ ዐላማ ያውቅ ነበር። ለዚህም ነው እግዚአብሔር ተቈጥቶ ይህን የባዕድ አማልክት ነቢይ የተቃወመው።

22፥23 ***አህያዪቱም የእግዚአብሔርን መልአክ ... ባየች ጊዜ፤*** ወደፊት የሚሆነውን ነገር በማወቅ የተደነቀው ሰው ለመንፈሳዊ እውነታ ዕውር ነበር፤ ነገር ግን ድዳ የሆነች አህያው የእግዚአብሔር መልአክ በመንገዱ ላይ ቆሞ አየች። የባዕድ አማልክት ነቢይ እንደመሆኑ፣ በለዓም የእንስሳን ጠባይ ለይቶ የማወቅ ችሎታ ነበረው፤ ሆኖም ለእርሱ ያልታየውን ነገር አህያው ልታይ ችላለች።

[29]በለዓምም መልሶ አህያዪቱን፣ "ስላላገጠሽብኝ ነዋ! በእጄ ሰይፍ ይዤ ቢሆን ኖሮ አሁኑኑ በገደልሁሽ ነበር" አላት። [30]አህያዪቱም ደግሞ በለዓምን እንዲህ አለችው፣ "ከብዙ ጊዜ ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ የተቀመጥክብኝ አህያህ አይደለሁምን? ታዲያ ይህን የመሰለ ነገር የማድረግ ልማድ ነበረኝ?"

እርሱም፣ "በጭራሽ!" አላት።

[31]በዚህ ጊዜ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የበለዓምን ዐይን ከፈተ፤ እርሱም *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) መልአክ የተመዘዘ ሰይፍ እንደ ያዘ መንገዱ ላይ ቆሞ አየ፤ ጐንበስ ብሎም በግንባሩ ተደፋ።

[32]*የእግዚአብሔርም* (ያህዌ) መልአክ እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ "አህያህን እንዲህ አድርገህ ሦስት ጊዜ የመታሃት ስለ ምንድን ነው? መንገድህ በፊቴ[a] ጠማማ ስለ ሆነ ልቃወምህ መጥቻለሁ። [33]አህያዪቱ አይታኝ ሦስቱንም ጊዜ ከፊቴ ዞር ባትልማ ኖሮ በእውነት እስካሁን አንተን በገደልሁህ አህያዪቱን ግን በሕይወት በተውኋት ነበር።

[34]በለዓምም *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) መልአክ፣ "ኀጢአት ሠርቻለሁ፤ እኔን ለመቃወም መንገዱ ላይ መቆምህን አላወቅሁም፤ አሁንም ደስ የማትሰኝ ከሆነ እመለሳለሁ" አለው።

[35]*የእግዚአብሔርም* (ያህዌ) መልአክ በለዓምን፣ "መሄዱን ከሰዎቹ ጋር ሂድ፤ ነገር ግን እኔ የምነግርህን ብቻ ተናገር" አለው። ስለዚህ በለዓም ከባላቅ አለቆች ጋር ሄደ።

[36]በለዓም በመምጣት ላይ መሆኑን ባላቅ በሰማ ጊዜ በግዛቱ ዳርቻ በአርኖን ወሰን ላይ ወደምትገኘው ወደ ሞዓብ ከተማ ሊቀበለው ወጣ። [37]ባላቅ በለዓምን፣ "በቶሎ እንድትመጣ ልኬብህ አልነበረምን? ለምን አልመጣህም? በእርግጥ ወሮታህን ልከፍል የማልችል ሆኜ ነውን?" አለው።

[38]በለዓምም፣ "ይኸው አሁን መጥቻለሁ፤ ግን እንዲያው ማንኛውንም ነገር መናገር እችላለሁን? እኔ መናገር የሚገባኝ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) በአፌ ያስቀመጠውን ብቻ ነው" ብሎ መለሰለት።

[39]ከዚያም በለዓም ከባላቅ ጋር ወደ ቂርያት ሐጾት ሄደ። [40]ባላቅም ከብቶችና በጎች ሠዋ፤ ከፊሉንም ለበለዓምና ከእርሱ ጋር ለነበሩት አለቆች ሰጣቸው። [41]በማግስቱ ጠዋት ባላቅ በለዓምን ወደ ባሞት በአል አወጣው፤ እዚያም ሆኖ ሕዝብ በከፊል አየ።

## የመጀመሪያው የበለዓም ንግር

**23** በለዓም፣ "እዚህ ሰባት *መሠዊያ ሥራ*ልኝ፤ ሰባት ኮርማዎችና ሰባት አውራ በጎችም አዘጋጅልኝ" አለው። [2]ባላቅም በለዓም እንደ ነገረው አደረገ፤ ሁለቱም በእያንዳንዱ መሠዊያ ላይ አንድ ኮርማና አንድ አውራ በግ አቀረቡ።

[3]ከዚያም በለዓም ባላቅን፣ "እኔ ወደዚያ ስሄድ፣ አንተ እዚሁ መሥዋዕትህ አጠገብ ቈይ፤ ምናልባትም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሊገናኘኝ ይመጣ ይሆናል፤ የሚገልጥልኝንም ሁሉ እነግርሃለሁ" አለው። ከዚያም በለዓም ወደ አንድ ገላጣ ኰረብታ ሄደ።

[4]እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ተገናኘው፤ በለዓምም፣ "እነሆ፤ ሰባት መሠዊያዎች አዘጋጅቻለሁ፤ በእያንዳንዱም ላይ አንድ ኮርማና አንድ አውራ በግ አቅርቤአለሁ" አለው።

[5]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) በበለዓም አፍ መልእክት አስቀምጦ፣ "ወደ ባላቅ ተመልሰህ ይህን መልእክት ንገረው" አለው።

[6]እርሱም ተመልሶ ሲሄድ ባላቅን ከመላው የሞዓብ አለቆች ጋር በመሠዊያው አጠገብ ቆሞ አገኘው። [7]ከዚያም በለዓም ንግሩን እንዲህ ሲል ጀመረ፤

"ባላቅ ከአራም አመጣኝ፣
 የሞዓብ ንጉሥ ከምሥራቅ ተራሮች።
'ና ያዕቆብን ርገምልኝ፤
 መጥተህም እስራኤልን አውግዝልኝ'
 አለኝ።

[a]32 የዚህ ጥገኛ ሐረግ የዕብራይስጡ ትርጒም አይታወቅም።

22፥29 ቊ33፤ ዘጸ25፥4፤ምሳ12፥10፤ 27፥23-27፤ማቴ 15፥19
22፥31 ዘፍ21፥19
22፥33 ቊ29
22፥34 ዘፍ39፥9፤ ዘኍ14፥40፤1ሳሙ15፥24፡30፤2ሳሙ12፥13፤24፥10፤ኢዮ33፥27፤ መዝ51፥4
22፥36 ቊ2፤ ዘኍ21፥13
22፥38 ዘኍ23፥5፡16፡26
22፥40 ዘኍ23፥1፡14፡29፤ሕዝ 45፥23
22፥41 ዘኍ21፥28፤23፥13
23፥1 ዘኍ22፥40
23፥2 ቊ14፡30
23፥3 ቊ15
23፥4 ቊ16
23፥5 ዘዳ4፥12፡ 4፥15፤ዘኍ22፥20፤ ኢሳ59፥21
23፥6 ቊ17
23፥7 ቊ18፤ዘፍ 24፥10፤ዘኍ22፥5፡6፤ 24፥3፡21፤ኢሱ24፥9፤ 2ሳሙ23፥1፤2ነገ5፥1፤ ነህ13፥2

22፥29 *በእጄ ሰይፍ ይዤ ቢሆን ኖሮ፣* ይህ አባባል ያሰበው ያልተሳካለትን የበለዓምን አስቂኝ ገጽታ ያመለክታል። በዚያ ቦታ ሰይፍ ነበረ (ቍ 23፥31-33 ይመ)፤ ሆኖም የሰይፉ ሰለባ መሆን የሚገባት አህያዪቱ አልነበረችም።

22፥31 *እግዚአብሔር የበለዓምን ዐይን ከፈተ፤* ይህ አባባል በቍ 28 መጀመሪያ ላይ ከተጠቀሰው ዐረፍተ ነገር ጋር አንድ ነው። በሌላ አንጻር በዚያ የቆመውን መልአክ ያይ ዘንድ የባዕድ አማልክት ነቢይ ዐይኖችን መክፈት የበለጠ ተአምር ነበር።

22፥35 *እኔ የምነግርህን ብቻ ተናገር፣* በለዓም አሁን በፊቱ ተደቅኖ ያለው ኀላፊነት ከባድ መሆኑን ይበልጥ መረዳቱን ያሳያል፤ እግዚአብሔር እንዲናገር የሚሰጠውንም ቃል ፈጽሞ ሊለውጥ አይችልም (23፥12፡20፡26)።

22፥37 *በቶሎ እንድትመጣ ልኬብህ አልነበረምን?* የታሪኩ አስቂኝ ክፍል ያሰበው ባልተሳካለት በበለዓም በኩል ብቻ ሳይሆን ግራ በተጋባው በባላቅም በኩል ነበር (23፥11፡ 25፤ 24፥10 ይመ)።

22፥40 *ባላቅም ከብቶችና በጎች ሠዋ፤* ለእግዚአብሔር የቀረበ መሥዋዕት አልነበረም። በለዓም የባዕድ አማልክት ነቢይ እንደ መሆኑ ጒበትን አይቶ ወደፊት የሚሆነውን የመተንበይ ችሎታ ነበረው፤ ስለዚህ ከተሰጠው ሥጋ ውስጥ ጒበት ሳይኖርበት አይቀርም። የእግዚአብሔር ቃለ ኀይል በእርሱ ላይ በመጣ ጊዜ በለዓም በተከታታይ የጥንቈላ ሥራውን አቋረጠ (24፥1)።

23፥1 *ሰባት መሠዊያ ... ሰባት ኮርማዎችና ሰባት አውራ በጎች፤* ይህ መሥዋዕት በለዓም እንደማያምንበት የባዕድ አምላክ አሠራር፣ እንደ አንዱ ክፍል ሆኖ ተዘጋጅቶ ነበር። ፍጹምነትን የሚያመለክተው ሰባት ቍጥር በአጠቃላይ በሴም ሕዝቦች ዘንድ ከፍተኛ ግምትና ትኩረት የሚሰጠው ነበር፤ ይህ ከምሥራቅ የመጣው ነቢይ የወደፊቱን ሁኔታ ለመተንበይ የሚያስችለው በቂ ጒበትና ሌላም የሥጋ ብልት ለመሥዋዕት ከሚቀርቡት ብዙ እንስሳት ያገኛል።

23፥2 *ባላቅም በለዓም እንደ ነገረው አደረገ፤* በለዓም ዋና አዛዥ ሲሆን፣ ባላቅ ግን አሁን ትእዛዝ ፈጻሚ ሆኖአል።

*23፥7-24፥24፤* በግጥም መልክ የቀረቡ ሰባት የትንቢት ስንኞች እዚህ ላይ ተጠቅሰዋል። የመጀመሪያው አራቱ ረዘም ያሉ ሲሆኑ ለትረካው መሸጋገሪያ የሆነ መግቢያ ያላቸውና ውበት የተላበሱ ቅኔያዊ ግጥሞች ናቸው (23፥7-10፡18-24፤ 24፥15-19)። የመጨረሻዎቹ ሦስቱ አጠር ያሉ ሲሆኑ በቀላሉ ለመረዳት የሚቻሉ አይደሉም፤ ነጠል ባለ ሁኔታም በተከታታይ ተጽፈው ይገኛሉ (24፥20፡21-22፡23-24)።

8እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ያልረገመውን፣
  እኔ እንዴት ረግማለሁ?
እግዚአብሔር (ያህዌ) ያላወገዘውንስ፣
  እንዴት አወግዛለሁ?
9ከዐለታማ ተራሮች ጫፍ ሆኜ
    አየዋለሁ፤
  በከፍታዎቹም ላይ ሆኜ
    እመለከተዋለሁ፤
ተለይቶ የሚኖረውን፣
  ራሱንም ከሌሎች ሕዝቦች ጋር
    የማይቈጥረውን፣
  ሕዝብ አያለሁ።
10የያዕቆብን ትቢያ ማን ቈጥሮ
    ይዘልቃል?
  የእስራኤልንስ ሩብ ማን
    ይቈጥረዋል።
የጻድቁን ሞት እኔ ልሙት፤
  ፍጻሜዬም የእርሱ ዐይነት ፍጻሜ
    ትሁን!"

11ባላቅም በለዓምን፣ "እንዴት እንዲህ ታደርገኛለህ? ጠላቶቼን እንድትረግምልኝ አመጣሁህ፤ አንተ ግን ባረክሃቸው እንጂ ምንም አላደረግህልኝም!" አለው።

12እርሱም መልሶ "እግዚአብሔር (ያህዌ) በአፌ ያስቀመጠውን መናገር አይገባኝምን?" አለው።

## ሁለተኛው የበለዓም ንግር

13ከዚህ በኋላ ባላቅ፣ "እነርሱን ማየት ወደ ምትችልበት ወደ ሌላ ቦታ እንሂድ፤ እዚያም ሁሉን ሳይሆን በከፊል ብቻ ታያቸዋለህ፤ እዚያም ሆነህ እነርሱን ርገምልኝ" አለው። 14ስለዚህም በፊስጋ ተራራ ጫፍ ላይ ወዳለው ወደ ጾፊም ሜዳ ወሰደው፤ እዚያም ሰባት መሠዊያ ሠርቶ በእያንዳንዱ ላይ አንድ ኮርማና አንድ አውራ በግ ሠዋ።

15በለዓምም ባላቅን፣ "እርሱን ለመገናኘት ወደዚያ ስሄድ፣ አንተ እዚሁ መሥዋዕትህ አጠገብ ቈይ" አለው።

16እግዚአብሔር (ያህዌ) በለዓምን ተገናኘው፤ በአፉም መልእክት አስቀመጠ፣ "ወደ ባላቅ ተመለስና ይህን መልእክት ንገረው" አለው።

17እርሱም ተመልሶ ሲሄድ ባላቅን ከመሳው የሞዓብ አለቆች ጋር በመሠዊያው አጠገብ ቆሞ አገኘው፤ ባላቅም፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ምን አለ?" ሲል ጠየቀው።

18ከዚያም ንግሩን እንዲህ ሲል ጀመረ፤

"ባላቅ ሆይ ተነሣ፤ አድምጠኝ፤
  የሴፎር ልጅ ሆይ ስማኝ፤
19ይዋሽ ዘንድ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ሰው
    አይደለም፤
  ይጸጸትም ዘንድ የሰው ልጅ
    አይደለም፤
ተናግሮ አያደርገውምን?
  ተስፋ ሰጥቶስ አይፈጽመውምን?
20እባርክ ዘንድ ትእዛዝ ተቀብያለሁ፤
  እርሱ ባርኳል፤ እኔም ልለውጠው
    አልችልም።
21"በያዕቆብ መጥፎ ነገር አልተገኘም፤
  በእስራኤልም* ጕስቍልና
    አልታየም፤
እግዚአብሔር አምላኩ (ያህዌ ኤሎሂም)
    ከእርሱ ጋር ነው፣
  የንጉሡም እልልታ በመካከላቸው
    ነው።
22እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ከግብፅ አወጣቸው፤
  ብርታታቸውም እንደ ጎሽ ብርታት
    ነው።
23በያዕቆብ ላይ የሚሠራ አስማት
    የለም፤
  በእስራኤልም ላይ የሚሠራ ሟርት
    አይኖርም፤
ለያዕቆብና ለእስራኤል፣
  'እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ያደረገውን እዩ!'
    ይባልላቸዋል።
24ሕዝቡ እንደ እንስት አንበሳ ይነሣል፤
  ያደነውን እስኪያነክት፣
የገደለውንም ደም እስኪጠጣ፣
  እንደማያርፍ አንበሳ ሆኖ ይነሣል።"

25በዚህ ጊዜ ባላቅ በለዓምን፣ "እንግዲያውስ ፈጽሞ አትርገማቸው፤ ፈጽሞም አትመርቃቸው!" አለው።

26በለዓምም፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚለኝን ሁሉ ማድረግ እንዳለብኝ አልነገርሁህምን?" ሲል መለሰለት።

*21 በያዕቆብ ላይ ወይም በእስራኤል ላይ እንከን አለማግኘቱን ያመለክታል።

23፥8 ቍ20፤ዘኍ 22፥12፤ኢሳ43፥13
23፥9 ዘፀ33፥16፤ ዘኍ22፥41፤ዘዳ32፥8
23፥10 ዘፍ13፥16፤ መዝ16፥3፤116፥15፤ ኢሳ 57፥1፤መዝ 37፥37
23፥11 ዘኍ22፥6፤ 24፥10፤ኢሱ24፥10፤ ነህ13፥2
23፥12 ዘኍ22፥18፡ 20
23፥13 ቍ27፤ዘኍ 22፥6፡41
23፥14 ቍ2፤ዘኍ 21፥20፤27፥12
23፥16 ዘፀ4፥15፤ ዘኍ22፥38
23፥17 ቍ6
23፥18 ቍ7፤ ዘኍ22፥2
23፥19 ዘፍ22፥17፤ ዘኍ11፥23፤1ሳሙ15 ፥29፤2ሳሙ7፥25፤ኢዮ 9፥32፤12፥13፤36፥5፤ መዝ33፥11፤89፥34፤ 102፥27፤110፥4፤119 ፥38፤ኢሳ55፥9፤ኤር 4፥28፤7፥16፤ሆሴ 11፥9፤9፤ሚል3፥6፤ ቲቶ1፥2፤ዕብ6፥18፤ 7፥21፤ያዕ1፥17
23፥20 ቍ5፡8፡16፤ ዘፍ22፥17፤ዘኍ22፥ 12፤24፥1፤ኢዮ9፥12
23፥21 ዘፍ26፥3፤ ዘፀ29፥45፡46፤ዘዳ 4፥7፤32፥15፤33፥5፤ መዝ32፥2፡5፤34፥17- 18፤85፥2፤89፥15-18፤ 145፥18፤ኢሳ33፥24፤ 40፥2፤44፥2፤ኤር50፥ 20፤ዘካ2፥10፤ሮሜ 4፥7-8
23፥22 ዘኍ24፥8፤ ኢሱ2፥10፤9፥9፤ዘዳ 33፥17፤ኢዮ39፥9፤ መዝ22፥21፤29፥6፤ 92፥10፤ኢሳ34፥7
23፥23 ቍ3፤ዘፍ 30፥27፤ዘኍ24፥1
23፥24 ዘፍ49፥9፤ ዘኍ24፥9፤ኢሳ49፥ 26፤ሕዝ19፥2፤ ናሆ2፥11

23፥8 *እግዚአብሔር ያልረገመውን እኔ እንዴት ረግማለሁ?* በለዓም ዋጋ ተከፍሎት እንዲያደርገው የሚጠበቅበትን ነገር ማድረግ አልቻለም። ከዓለም ሕዝብ ለየት ያለውን (ቍ 9) የእግዚአብሔርን ሕዝብ በለዓም እንዳይረግም እግዚአብሔር ራሱ ከለከለው።

23፥10 *የጻድቁን ሞት እኔ ልሙት፤* በለዓም ያልፈጸመው ከንቱ ምኞት ነው (31፥18፡16 ይመ)። *ፍጻሜዬም የእርሱ ዐይነት ፍጻሜ ትሁን፤* እንዲረግም የመጣው ሰው ከእስራኤል በረከት ተካፋይ ይሆን ዘንድ ተመኘ።

23፥13 *ሁሉንም ሳይሆን በከፊል ብቻ፤* እጅግ ከፍተኛ የሆነው ቍጥራቸው በግልጽ የማይታይበትን ቦታ በመምረጥ ባላቅ የእስራኤልን ኀይል ዝቅ ለማድረግ ሞከረ። እሱ እንዳሰበው ሳይሆን፣ በኋላ የተነገረው የትንቢት ቃል (ቍ 18-24) እስራኤልን በመባረክ የበለጠ ሆኖ ተገኝቶአል።

23፥19 *ይዋሽ ዘንድ እግዚአብሔር ሰው አይደለም፤* እነዚህ ድንቅ ቃላት፣ እግዚአብሔር የማይለወጥና ቃሉ የታመነ መሆኑን ይገልጻሉ። በለዓም የእግዚአብሔርን ዕቅድ የሚያደናቅፍ ወላዋይ፣ እውነተኛውን ነገር የሚያጣምምና ተለዋዋጭ ባሕርይ ያለው በመሆኑ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል ላለው ልዩነት ጥሩ ምሳሌ ነው።

23፥21 *የንጉሡም እልልታ በመካከላቸው ነው፤* ከሙሴ መጽሐፍ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ ስለ እግዚአብሔር ንጉሥነት በግልጽ የሚያሳይ ሐሳብ በበለዓም መነገሩ፣ ይሆናል ተብሎ የማይታሰብ ነገር ነው። እግዚአብሔር ኀያል ንጉሥ በመሆኑ፣ በሚያስገርምና በሚያስደንቅ ሁኔታ የእግዚአብሔርን ሕዝብ እንዲባርክ በለዓምን ለዐላማው ሊጠቀምበት ችሎአል።

23፥22 *ጎሽ፤* በጥንት የቅርብ ምሥራቅ አገሮች ባሕል መሠረት ኀይልን የሚያመለክት ቃል ነው (24፥8 ይመ)።

23፥23 *በያዕቆብ ላይ የሚሠራ አስማት የለም፤* በለዓም ካየው አስፈሪ ሁኔታ የተነሣ የተናገረው ነው። እግዚአብሔር እስራኤልን መባረኩን ሊቋቋም የሚያስችለው ዘዴ በለዓም ከማታለያ ከረጢቱ ውስጥ ሊያወጣ አልቻለም።

23፥24 *እንደ እንስት አንበሳ፤* እንስት አንበሳ በአደን ጊዜ እንደምታደርገው ሁሉ፣ እስራኤል ተነሥቶ ጠላቱን ሊውጥ እንደተዘጋጀ ያመለክታል (24፥9፤ ዘፍ 49፥9 ይመ)።

## ሦስተኛው የበለዓም ንግር

[27]ከዚህ በኋላ ባላቅ በለዓምን፣ "በል እንግዲያው ወደ ሌላ ቦታ ልውሰድህ፤ ከዚያ ሆነህ እንድትረግምልኝ ምናልባት እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ይፈቅድልህ ይሆናል" አለው:: [28]ባላቅም በለዓምን ምድረ በዳው ቍልቍል ወደሚታይበት ወደ ፌጎር ጫፍ አወጣው::

[29]በለዓምም፣ "ሰባት መሠዊያዎች እዚህ ሥራልኝ፤ ሰባት ኮርማዎችና ሰባት አውራ በጎችም አዘጋጅልኝ አለው:: [30]ባላቅም በለዓም እንደ ነገረው አደረገ፤ በእያንዳንዱም መሠዊያ ላይ አንድ ኮርማና አንድ አውራ በግ ሠዋ::

**24** በለዓምም እግዚአብሔር (ያህዌ) እስራኤልን መባረክ እንደ ወደደ ባየ ጊዜ፣ እንደ ሌላው ጊዜ ሁሉ አስማት ለመሻት አልሄደም፤ ነገር ግን ፊቱን ወደ ምድረ በዳ መለሰ:: [2]በለዓም አሻግሮ ተመልክቶ እስራኤል በየነገድ በየነገዱ ሆኖ መስፈሩን ሲያይ የእግዚአብሔር (ኤሎሂም) መንፈስ በላዩ መጣበት፤ [3]ንግሩንም እንዲህ ሲል ጀመረ፤

"የዚያ ዐይኑ የተከፈተለት፣
የቢዖር ልጅ የበለዓም ንግር፣
[4]የዚያ የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ቃል
የሚሰማ፣
ሁሉን የሚችል[ሀ] የአምላክን ራእይ
የሚያይ፣
ከመሬት የተደፋው ዐይኖቹም
የተከፈቱለት ሰው ንግር፤

[5]"ያዕቆብ ሆይ፤ ድንኳኖችህ፣
እስራኤል ሆይ፤ ማደሪያዎችህ
እንዴት ያማሩ ናቸው!

[6]"እንደ ሸለቆዎች፣
በወንዝ ዳር እንዳሉም የአትክልት
ስፍራዎች ተዘርግተዋል፤
በእግዚአብሔር (ያህዌ) እንደ ተተከሉ
ሬቶች፣
በውሃም አጠገብ እንዳሉ ዝግባዎች
ናቸው::
[7]ከማድጋቸው ውሃ ይፈሳል፤
ዘራቸውም የተትረፈረፈ ውሃ
ያገኛል፤

"ንጉሣቸው ከአጋግ ይልቃል፤
መንግሥታቸውም ከፍ ከፍ ይላል፤

[8]"እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ከግብፅ አወጣቸው፤
ብርታታቸውም እንደ ጎሽ ብርታት
ነው፤
ጠላቶች የሆኑአቸውን ሕዝብ
ያነክታሉ፤
ዐጥንቶቻቸውን ያደቅቃሉ፤
በፍላጻቸው ይወጓቸዋል::
[9]እንደ አንበሳ አድፍጠዋል፤
እንደ እንስቲቱም አንበሳ
አድብተዋል፤
ሊቀሰቅሳቸውስ የሚችል ማን ነው?

"የሚባርኩህ ቡሩክ፣
የሚረግሙህም ርጉም ይሁኑ!"

[10]ከዚያም ባላቅ፣ በበለዓም ላይ እጅግ ተቈጣ፤ እጆቹንም አጨብጭቦ እንዲህ አለው፤ "ጠላቶቼን እንድትረግምልኝ ጠራሁህ፤ አንተ ግን ሦስቱንም ጊዜ ባረክሃቸው:: [11]በል ቶሎ ወደ ቤትህ ሂድልኝ፤ ወሮታህን አሳምሬ ልከፍልህ ነበር፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ግን እንዳታገኝ ከለከለህ::"

[12]በለዓምም ለባላቅ እንዲህ ሲል መለሰለት፤ ወደ እኔ ለላክሃቸው ሰዎች እንዲህ ብዬ ነግሬአቸው አልነበረምን? [13]'ሌላው ይቅርና ባላቅ በብርና በወርቅ የተሞላ ቤት መንግሥቱን ቢሰጠኝ እንኳ፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚለውን ብቻ ከመናገር በስተቀር ከእግዚአብሔር (ያህዌ) ትእዛዝ ውጭ በራሴ

[ሀ]4 በዕብራይስጥ ሻዳይ ማለት ነው::

23፥26 ዘኍ22፥18፡20
23፥27 ቍ13፤ ዘኍ24፥10
23፥28 ዘኍ25፥3፡18፤31፥16፤ዘዳ3፥29፤4፥3፤ኢሱ22፥17፤መዝ106፥28፤ሆሴ9፥10
23፥30 ቍ2
24፥1 ዘኍ23፥20፡23፡28
24፥2 ዘኍ11፥25፡26
24፥3 ቍ15
24፥4 ዘፍ15፥1ዘኍ22፥9
24፥5 ኤር4፥20፤30፥18፤ሚል2፥12
24፥6 ዘፍ2፥10፤ ኢዮ 29፥19፤መዝ1፥3፤45፥8፤104፥16፤ ማሕ4፥14ሕዝ31፥5
24፥7 ዘፀ17፥8-16፤ ዘዳ28፥1፤2ሳሙ5፥12 ፤1ዜና14፥2፤መዝ89፥27፤145፥11-13
24፥8 ዘፀ15፥6፤ 2ሳሙ18፥14፤መዝ45፥5፤ኤር50፥17
24፥9 ዘፍ12፥2፡3፤ ዘኍ23፥24
24፥10 ቍ3-9፤ዘፀ4፥14፤ዘኍ22፥6፤23፥7-10፡11፡18-24፤ዘዳ23፥5፤ኢዮ27፥23፤34፥37፤ሰቆ2፥15፤ሕዝ21፥14፤22፥13፤25፥6
24፥11 ቍ14፡25፤ ዘኍ22፥17
24፥12 ዘኍ22፥18
24፥13 ዘኍ22፥18፡20

23፥28 *ፌጎር፤* በለዓም የእስራኤልን ሰፈር በሚገባ ለማየት የቻለበት (24፥2) የተራራው ሰንሰለት ሰሜናዊ ክፍል ነው (የ23፥14 ማብ ይመ)::

24፥1 *እንደ ሌላው ጊዜ ሁሉ አስማት ለመሻት፤* እዚህ ላይ የበለዓም የጥንቈላና የአስማት ሥራ ተገልጾአል (የ22፥40፤ 23፥1 ማብ ይመ)::

24፥2 *የእግዚአብሔር መንፈስ በላዩ መጣበት፤* የእግዚአብሔር መንፈስ በበለዓም ላይ መምጣቱ በአዲስ ኪዳን ከተገለጸው በመንፈስ ቅዱስ መሞላት ጋር ተመሳሳይ አይደለም (ሐሥ 2፥1-4):: መንፈስ ቅዱስ በላዩ ላይ የመጣው በለዓም ትክክለኛ የእግዚአብሔር ነቢይ እንደ ሆነ ለማጽደቅ ሳይሆን፣ በእርሱ በኩል አንድ ጊዜ የሚገልጠው እውነት በመኖሩ ነው:: እግዚአብሔር ዐላማውን ለመፈጸም ሲል አንዳንድ ጊዜ እርሱን በሚገባ የማያውቁትንና በመንገዱ የማይሄዱትን ሰዎች ይጠቀምባቸዋል::

*24፥3-4፤* ለትንቢቱ እንደ መግቢያ ሆኖ ሰፋ ተደርጎ የተጻፈው ሐሳብ፣ ህልዎተ እግዚአብሔር በበለዓም ፊት በመሆኑ ያየውንና የተረዳውን ነገር የሚገልጽ ነው:: አሁን የበለዓም ዐይኖች ተከፍተዋል (የ22፥31 ማብ ይመ)::

*24፥6-7፤* እዚህ ላይ በአጠቃላይ መልኩ በለዓም የሚናገር ሲሆን፣ እስራኤል በተሰጣቸው አዲስ ምድር በሚሰፍሩበት ጊዜ ወደ እነርሱ የሚመጣው በረከት የተትረፈረፈ እንደሚሆን ያመለክታል:: ከእግዚአብሔር የሚሰጣቸው እንዲህ ዐይነቱ የተትረፈረፈ በረከት፣ በኤድን የነበረውን በረከት የሚያስታውስ ነው::

24፥7 *ከአጋግ ይልቃል፤* የንጉሥ ሳኦል ጠላት የሆነውን ሰው በሚመለከት (1ሳሙ 15፥32-33) የተነገረ፣ ወደ ፊት የሚፈጸም አንድ ትንቢት ሊሆን ይችላል፤ ይህም በአራተኛው ትንቢት ውስጥ የተጠቀሱትን (ቍ 15-19) አስደናቂ ቃሎችን ለመግለጽ የሚያዘጋጅ መንደርደሪያ ሆኖ የገባ ሐሳብ ነው:: ነገር ግን አጋግ የሚለው ስም በአማሌቃውያን ነገሥታት ዘንድ የተለመደ ነው፤ ይኸውም የሚያመለክተው እስራኤላውያን ከግብፅ በወጡ ጊዜ (ዘፀ 17፥8-13)፣ ከዚያም ቀጥሎ ከነዓን ለመግባት በተቃረቡበት ወቅት (14፥45 ይመ)፣ በእነርሱ ላይ ጦርነት የከፈቱባቸውን አማሌቃውያንን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል::

24፥8 *እግዚአብሔር ከግብፅ አወጣቸው፤* የእስራኤልን ድነት የሚያመለክቱ እነዚህ ቍልፍ የሆኑ ቃሎች ጠላታቸው በሆነ የሌላ አገር ሰው ተነግረዋል (የ25፥1 ማብ ይመ)::

24፥9 *የሚባርኩህ ቡሩክ፣ የሚረግሙህም ርጉም፤* ለአብርሃም በተሰጠው ተስፋ ውስጥ የተጠቀሰው የበረከትና የመርገም ቃል (ዘፍ 12፥2-3)፣ የእስራኤልን መባረክ አስመልክቶ በተነገረው በዚህ ትንቢትም ውስጥ ተገልጾአል:: እዚህ ላይ በለዓም የእስራኤላውያን በረከት ተካፋይ ለመሆን ያለውን ምኞት አስረግጦ መናገሩ ይሆናል (የ23፥10 ማብ ይመ)::

24፥11 *እግዚአብሔር ግን እንዳታገኝ ከለከለህ፤* እስራኤልን በለዓም ስላልረገመለት ባላቅ በመከፋቱ፣ በለዓምን ያለ አንዳች ክፍያ ሸኘው፤ ይኸውም በለዓም ጓጉቶለት ለነበረው ዋጋ በምላሹ የተሰጠው እጅግ አሳፋሪ ስድብ ነው (2ጴጥ 2፥15 ይመ)::

ሐሳብ በጎም ሆነ ክፉ ማድረግ አልችልም።'
14እንግዲህ ወደ ሕዝቤ እመለሳለሁ፤ ይሁን እንጂ በሚመጣው ዘመን ይህ ሕዝብ በሕዝብህ ላይ የሚያደርገውን ና ልንገርህ።"

## አራተኛው የበለዓም ንግር

15ከዚያም እንዲህ ሲል ንግሩን ጀመረ፤

"የቢዖር ልጅ የበለዓም ንግር፤
የዚያ ዐይኑ የተከፈተለት ሰው
ንግር።
16የዚያ የልዑልን (ኤሎሂም) ቃል የሚሰማ፣
ከልዑልም ዕውቀትን ያገኘው፣
ሁሉን ከሚችለው ራእይ
የሚገለጥለት፣
መሬት የተደፋው፣ ዐይኖቹም
የተገለጡለት ሰው ንግር፤

17"አየዋለሁ፤ አሁን ግን አይደለም፤
እመለከተዋለሁ፤ በቅርቡ ግን
አይደለም፤
ኮከብ ከያዕቆብ ይወጣል፤
በትረ መንግሥት ከእስራኤል
ይነሣል።
የሞዓብን ግንባሮች፣
የሤትንም ወንዶች ልጆች ራስ
ቅል✝ ያደቃል።
18ኤዶም ይሸነፋል፤
ጠላቱ ሴይርም ድል ይሆናል፤
እስራኤል ግን እየበረታ ይሄዳል።
19ገዥ ከያዕቆብ ይወጣል፤
የተረፉትንም የከተማዪቱን ነዋሪዎች
ይደመስሳል።"

## የመጨረሻዎቹ የበለዓም ንግሮች

20ከዚያም በለዓም አማሌቅን አይቶ ንግሩን እንዲህ ሲል ጀመረ፤

"አማሌቅ ከሕዝቦች የመጀመሪያው
ነበር፤
በመጨረሻ ግን ይደመሰሳል።"

21ቄናውያንንም አይቶ ንግሩን እንዲህ ሲል ጀመረ፤

"መኖሪያህ አስተማማኝ ነው፤
ጎጆህም በዐለት ውስጥ ተሠርቶአል፤
22ያም ሆኖ ግን እናንት ቄናውያን፤
አሶር በምርኮ ሲወስዳችሁ
ትደመሰሳላችሁ።"

23ከዚያም ንግሩን ቀጠለ፤

"አቤት! ሰምባከ (ኤሎሂም) ይህን
ሲያደርግ ማን ይተርፋል?
24መርከቦች ከኪቲም ዳርቻዎች
ይመጣሉ፤
አሦርንና ዔቦርን ይይዛሉ፤
እነርሱም ደግሞ ይደመሰሳሉ።

25ከዚህ በኋላ በለዓም ተነሥቶ ወደ ቤቱ ተመለሰ፤ ባላቅም መንገዱን ቀጠለ።

## ሞዓብ እስራኤልን አሳሳተ

25 እስራኤላውያን በሰጢም በነበሩበት ጊዜ ወንዶቹ ከሞዓብ ሴቶች ጋር ማመንዘር ጀመሩ። 2እነዚህም ሴቶች ወደ አምላኮቻቸው መሥዋዕት ሕዝቡን ጋበዙ፤ ሕዝቡም መሥዋዕቱን በላ፤ ለአማልክቱም ሰገደ።

3ስለዚህ እስራኤል የፌጎርን በኣል በማምለክ ተባበረ፤ የእግዚአብሔርም (ያህዌ) ቍጣ በላዩ ነደደ።

4እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፣ "እስፈሪው የእግዚአብሔር (ያህዌ) ቍጣ ከእስራኤል እንዲመለስ የሕዝቡን አለቆች ሁሉ ወስደህ ግደልና በጠራራ ፀሓይ ላይ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ስቀላቸው" አለው።

24፥14 ዘፍ49፥1፤ ዘኍ31፥8፡16፤ሚክ 6፥5
24፥16 ዘፍ14፥18፤ ዘኍ22፥9፤ኢሳ14፥14
24፥17 19፥37፤ዘፍ 49፥10፤ዘኍ21፥29፤ ዘዳ23፥6፤ኢሳ15፥1-16፥14፤ኤር48፥45፤ ማቴ2፥2፤ራእ1፥7
24፥18 ዘፍ9፥25፤ 14፥6፤ዘዳ1፥44፤ኢሱ 12፥7፤15፥10፤መሳ 5፥4፤2ሳሙ8፥12፤ 1ዜና18፥11፤መዝ 60፥8፤ኢሳ11፥14፤ አሞ9፥12፤አብ1፥2
24፥19 ዘፍ49፥10፤ ሚክ 5፥2
24፥20 ዘፍ14፥7፤ ዘፀ17፥14፤ዘዳ25፥19፤ 1ሳሙ15፥20፤30፥17-20፤2ሳሙ8፥12፤ 1ዜና18፥11
24፥21 ዘፍ15፥19፤ መዝ37፥27፤ምሳ1፥33 ፤ኢሳ32፥18፤ሕዝ 34፥27
24፥22 ዘፍ10፥22
24፥24 ቍ20፥22፤ ዘፍ10፥4፤21
24፥25 ዘኍ22፥5
25፥1 ዘፍ19፥37፤ ዘኍ21፥16፤31፥16፤ ኢሱ2፥1፤ኢሳ66፥11፤ ኤር5፥7፤7፥9፤9፥2፤ ኢል3፥18፤ሚክ6፥5፤ 1ቆሮ10፥8፤ራእ2፥14
25፥2 ዘፀ20፥5፤ 32፥6፤ዘዳ32፥38፤ 1ቆሮ10፥20
25፥3 ዘኍ23፥28፤ ዘዳ4፥19፤መሳ2፥19፤ 1ነገ9፥9፤ኤር1፥16፤ 44፥3
25፥4 ዘፀ32፥12፤ ዘኍ7፥2፤13፥3፤ዘዳ4፥3 ፤13፥17፤ኢሱ7፥26፤ 2ሳሙ21፥6፤2ነገ23፥26፤2ዜና28፥11፤29፥10፤30፥8፤ዕዝ10፥14፤ኤር44፥3

✝17 የአራተ ሳምራውያኑ ቅጅ የራስ ቅል ሲል፣ በማሶሬቲክ ቅጅ ግን ያቃሉ ትርጕም አይታወቅም።

24፥14 *በሚመጣው ዘመን፤* ይህ አገላለጽ ይበልጡን ገና በሩቅ ያለውን (መሲሑ የሚመጣበትን) የወደፊቱን ዘመን ያመለክታል (ኤር 48፥47 እና ማብ ይመ)።

*24፥15-16፤* በሦስተኛው ትንቢት መጀመሪያ ላይ እንደ ተጠቀሰው ሁሉ (ቍ 3-4 ይመ)፣ ለአራተኛው ትንቢት የተጻፈው መግቢያም እንደዚሁ ረጅም ነው፤ ይህም በዚህ ትንቢት ውስጥ የተጠቀሱ አስደናቂ ቃሎች አንባቢ እንዲረዳ የሚያዘጋጅ ነው።

24፥17 *ኮከብ ... በትረ መንግሥት፤* መጀመሪያ ዳዊት በነገሠ ጊዜ ተፈጽሞ ይሆናል፤ በከፍተኛ ሁኔታ ሙሉ በሙሉ የሚፈጸመው ግን በመጨረሻ መሲሑ መጥቶ በሚገዛበት ጊዜ ነው። ወደ ፊት እስራኤልን የሚታደገው እንደ ኮከብ (ራእ 22፥16) እና በንጉሥ እንዳለች የከበረች በትር ይሆናል፤ በሕዝቡም ጠላቶች ላይ ድል ይቀዳጃል (ቍ 19 ይመ)። *ሤት፤* በጥንታዊ የግብፅ መዛግብት ውስጥ ሹቱ በመባል ይታወቁ የነበሩት የመጀመሪያዎቹ (ጥንታውያን) የሞዓብ ነዋሪዎች ሊሆኑ ይችላሉ።

24፥20 *አማሌቅ... የመጀመሪያው ነበር፤* በእስራኤል ላይ ጦርነት ለመክፈትና እግዚአብሔር በሕዝቡ ላይ ያለውን ዐላማ ለመቃወም የመጀመሪያው ነገድ ነበር (ዘፀ 17፥8-13)።

24፥21 *ቄናውያንንም፤* ይህ ስም ብረታ ብረት ሠራተኞች የሆኑትን ነገዶች ያመለክታል፤ በሌላ ቦታ ቄናውያን ከእስራኤል ጋር እንደተባበሩ ተገልጾአል (መሳ 1፥16፤ 4፥11፤ 1ሳሙ 15፥6 ይመ)። የሙሴ ዐማት ቄናዊ ቢሆንም ከምድያም ጋር ተባብሮአል (ዘፀ 2፥16 ይመ)፤ ምናልባትም በለዓም የተናገረውም ስለ ምድያማውያን ሳይሆን አይቀርም (22፥4:7 ይመ)።

24፥24 *ኪቲም፤* በቆጵሮስ የነበረችው ጥንታዊቷ ኪቶን ልትሆን ትችላለች። *አሦርንና ዔቦርን ይይዛሉ፤ እነርሱም ደግሞ ይደመሰሳሉ፤* አንድ ሕዝብ ተነሥቶ የሌላውን አገር ይወስዳል፤ እርሱም ደግሞ መጨረሻው ጥፋት ይሆናል። በአንጻሩም ለእስራኤል ሕዝብ የሚሆነው የማያቋርጥ በረከት፣ የመጨረሻውን ድል በመቀዳጀት (ቍ 17-19) ታዳጊያቸው የሆነው ወደፊት የሚሰጣቸውን አስተማማኝ ተስፋ ያመለክታል።

*25፥1-18፤* ም 31፥8:16 እስከምንደርስ ድረስ፣ ለእስራኤል መሳሳት ዋና ምክንያት የሆነው በለዓም እንደ ነበር አንረዳም (የ22፥5:8 ማብ ይመ)። በለዓም የርግማን ቃል በመናገር እስራኤልን ማጥፋት አልቻለም፤ ነገር ግን በከነዓናውያን የበኣል ልምላሜ ሥርዐት እስራኤልን አታለለ።

25፥1 *ሰጢም፤* ከነዓንን ድል ለማድረግ እስራኤል ዝግጅት ያደረገችበት ቦታ ሌላ ስሙ ነው፤ የሚገኘውም ከዮርዳኖስ ወንዝ ማዶ፣ ከጥንታዊቷ የኢያሪኮ ከተማ ትይዩ ነበር (ኢሱ 2፥1 ይመ)። *ማመንዘር ጀመሩ፤* እስራኤል የበኣልን የልምላሜ ሥርዐት ተቀብላ የዝሙት ኀጢአት ከማድረጓም በላይ፣ በምድሪቱ ለነበሩ ባዕድ አማልክት መስገዷና (ቍ 2-3) በታሪካቸው ውስጥ በሕዝቡ ኀጢአት ተሳታፊ ሆና በመገኘቷ ከእግዚአብሔር ጋር የገባችውን ኪዳን ጣሰች።

25፥4 *ወስደህ ግደልና በጠራራ ፀሓይ ላይ በእግዚአብሔር ፊት ስቀላቸው፤* የሞቱት ሰዎች በድን በዚህ ሁኔታ እንዲታይ መደረጉ፣ በኀጢአት ምክንያት ከቅጣት የተረፉትን ሰዎች ያስጠነቅቃል።

[5]ሙሴም የእስራኤልን ዳኞች፣ "እያንዳ ንዳችሁ የፌጎርን በአል በማምለክ የተባበሩ ትን ሰዎቻችሁን ግደሉ አላቸው።"

[6]ከዚህ በኋላ ሙሴና መላው የእስራኤል ማኅበር በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ላይ እያለቀሱ ሳለ፣ አንድ እስራኤላዊ እነርሱ እያዩት አንዲት ምድያማዊት ሴት ይዞ ወደ ቤተ ሰቡ መጣ። [7]የካህኑ የአሮን ልጅ የአልዓዛር ልጅ ፊንሐስ ይህን ባየ ጊዜ ማኅ በሩን ትቶ ጦሩን በእጁ በመያዝ፣ [8]እስራ ኤላዊውን ተከትሎ ወደ ድንኳኑ ገባ፤ ጦሩ ንም ወርውሮ እስራኤላዊውንና ሴቲቱን አጣምሮ ወጋቸው፤ ከዚያም በእስራኤላው ያን ላይ የወረደው መቅሠፍት ተከለከለ፤ [9]ሆኖም በመቅሠፍቱ የሞተው ሰው ቍጥር ሃያ አራት ሺህ ደርሶ ነበር።

[10]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [11]"የካህኑ የአሮን ልጅ፣ የአልዓዛር ልጅ ፊንሐስ እኔ ለክብሬ በመካከላቸው እንደ ምቀና ስለ ቀና ቍጣዬን ከእስራኤላውያን መልሶታል፤ ስለዚህ እኔም በቅናቴ ጨርሶ አላጠፋኋቸውም፤ [12]ስለዚህ እነሆ እኔ የሰላም ቃል ኪዳኔን ከእርሱ ጋር እንደማደርግ ንገ ረው። [13]ስለ አምላኩ (ኤሎሂም) ክብር ቀንቶ ለእስ ራኤላውያን ስላስተሰረየላቸው፣ እርሱና ልጆቹ ዘላቂ የክህነት ቃል ኪዳን ይኖራቸዋል።

[14]ከምድያማዊቷ ሴት ጋር የተገደለው እስራኤላዊ የሰሉ ልጅ ዘንበሪ ይባላል፤ የስ ምዖናውያን ቤተ ሰብ አለቃ ነበር። [15]እንዲ ሁም የተገደለችዋ ምድያማዊት ሴት ከስቢ ትባላለች፤ እርሷም ከምድያማውያን ቤተ ሰብ የአንዱ ነገድ አለቃ የሆነው የሱር ልጅ ነበረች።

[16]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤

25፥5 ዘፀ32፥27፤ ሆሴ9፥10
25፥6 ዘፍ25፥2፤ ዘኍ14፥1፤መሳ2፥4፤ ሩት1፥9፤1ሳሙ11፥4፤ 2ሳሙ15፥30፤ዕዝ 10፥1፤መዝ126፥6፤ ኢር41፥6
25፥7 ዘፀ6፥25፤ኢሱ 22፥13፤መሳ5፥8፤20፥ 28፤1ሳሙ13፥19፥22፤ 1ነገ18፥28፤መዝ35፥3 ፤46፥9፤ኢል3፥10፤ ሚክ4፥3
25፥8 መዝ106፥30
25፥9 ዘኍ14፥37፤ 31፥16፤1ቆሮ10፥8
25፥11 ዘፀ20፥5፤ዘዳ 32፥16፥21፤መዝ 78፥58፤106፥30
25፥12 ኢሳ11፥9፤ 54፥10፤ሕዝ34፥25፤ 37፥26፤ሚል2፥4፥5
25፥13 ቍ11፤ዘፀ 29፥9፥36፤1ነገ19፥10፤ 2ነገ10፥16፤መዝ106፥ 31፤ኢር33፥18፤ሮሜ 3፥25
25፥14 ቍ6፤ ዘኍ1፥6
25፥15 ቍ18፤ዘኍ 31፥8፤ኢሱ13፥21፤ ዕን3፥7
25፥16 ዘኍ31፥7
25፥17 ዘፀ23፥22፤ ዘኍ31፥1-3፤ዘዳ21፥1 ፤መሳ2፥16-18፤1ሳሙ 17፥9፥35፤2ነገ9፥27፤መዝ 8፥2፤21፥8፤74፥23
25፥18 ዘኍ23፥28
26፥1 ዘኍ14፥37፤ 25፥8
26፥2 ዘፀ30፥11- 16፤ዘኍ1፥3
26፥3 ቍ63፤ዘኍ 22፥1፤33፥48፤

[17]"ምድያማውያንን እንደ ጠላት ቍጠራችሁ ፍጇቸው። [18]ይኸውም ፌጎር ላይ በተፈጸመው ድርጊትና በፌጎር ምክንያት በመጣው መቅ ሠፍት በተገደለችው በምድያማዊው አለቃ ልጅ፣ በእኅታቸው በከስቢ አታልለው የጠላ ትነት ሥራ ስለሠሩባችሁ ነው።"

## ሁለተኛው የሕዝብ ቈጠራ

**26** ከመቅሠፍቱ በኋላ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴንና የካህኑን የአሮንን ልጅ አልዓዛርን እንዲህ አላቸው፤ [2]"ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያ በላይ የሆናቸውን፣ በእ ስራኤልም ጦር ሰራዊት ውስጥ ለማገልገል ብቃት ያላቸውን ሁሉ ከመላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ ከየቤተ ሰቡ ቍጠሩ።" [3]ስለዚህ ሙሴና ካሁ አልዓዛር ከኢያሪኮ* ማዶ በዮር ዳኖስ አጠገብ ባለው በሞዓብ ሜዳ ለሕዝቡ እንዲህ ሲሉ ተናገሩ፤ [4]"እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ዕድሜያቸው ሃያና ከዚያ በላይ የሆነውን ቍጠሩ።"

ከግብፅ የወጡት እስራኤላውያንም እነዚህ ነበሩ፤

[5]የእስራኤል የበኵር ልጅ የሆነው የሮቤል ዘሮች እነዚህ ነበሩ፤

በሄኖን በኩል፣ የሄኖኀውያን ጐሣ፤
በፈለስ በኩል፣ የፈሉሳውያን ጐሣ፤
[6]በአስሮን በኩል፣ የአስሮናውያን ጐሣ፤
በከርሚ በኩል፣ የከርማውያን ጐሣ፤

[7]እነዚህ የሮቤል ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህም የተቈጠሩት አርባ ሦስት ሺህ ሰባት መቶ ሠላሳ ነበሩ።

ኢሱ13፥32 26፥4 ዘፀ6፥14፤13፥3 26፥5 ዘፍ46፥9፤ዘኍ1፥20፤ 1ዜና5፥3 26፥6 ዘፍ46፥9፤1ዜና5፥3

*3 በዕብራይስጥ የኢያሪኮ ዮርዳኖስ የሚባል ሲሆን፣ ይህም የዮርዳኖስ ወንዝ የጥንት ስም ሳይሆን አይቀርም።

25፥6 *አንዲት ምድያማዊት ሴት ይዞ ወደ ቤተ ሰቡ መጣ*። ዘንበሪና ፍቅረኛው ከስቢ (ቍ 15)፣ ለእግዚአብሔር ቃልና ለቅ ድስና ያሳዩት ንቀት፣ ሞት ይደረጋል ተብሎ የማይገመት ነበር።

25፥9 *ሃያ አራት ሺህ*፤ ሕዝቡ በአልን በማምለክ የድፍረት ኀጢአት ስለ ሠሩ የሞቱት ሰዎች ቍጥር ሲሆን፣ ይህም በቆ ሬና በተባባሪዎቹ ዐመፅ የተነሣ ከሞቱት ሰዎች ቍጥር ይበል ጣል (14000፤ 16፥49 ይመ)። የሞቱት ሰዎች ቍጥር ከፍተኛ ነት፣ በመጀመሪያው (1፥46) እና በሁለተኛው (26፥51) የሕዝብ ቈጠራ ከተገለጸው ቍጥሩ እጅግ ብዙ ከሆነው ሕዝብ ጋር ሲነጻ ጸር ተመጣጣኝነት አለው።

25፥11 *ለክብሬ በመካከላቸው እንደምቀና ስለ ቀና*፤ ከዘፀ 20፥4-6 ጋር ያነጻጽሩ፤ ፊንሐስ ለእግዚአብሔር ክብር በመ ቅናቱ እውነተኛ የእግዚአብሔር ካህናት ሆነው ያገለግሉት ዘንድ እግዚአብሔር ከፊንሐስና ከዘሩ ጋር ኪዳን አደረገ (የዘፍ 9፥9 ማብ ይመ)። የአልዓዛር ልጅ ፊንሐስ ያደረገው ነገር፣ አጎ ቶቹ የሆኑት ናዳብና አብዩድ የፈጸሙትን የግዴለሽነት ኀጢአት ይቃረናል (ዘሌ 10፥1-3 እና ማብ ይመ)።

25፥17 *ምድያማውያንን እንደ ጠላት ቍጠራችሁ ፍጇ ቸው*፤ ይህ የተፈረደባቸው እስራኤልን ለማሳት በተደረገው ተን ኮል ውስጥ ተሳታፊ ስለ ነበሩ ነው። እስራኤልን ለመቋቋም በተ ደረገው ሤራ ከመጀመሪያ ጀምሮ ምድያማውያን ከባላቅ ጋር በመተባበራቸው (22፥4፡7)፤ በ 31፥1-24 ላይ ለተገለጸው ቅዱስ ጦርነት ዒላማዎች ሆኑ።

*26፥1-51፤* ከሠላሳ ስምንት ዓመት በፊት ለድል ጦርነት እንዲወጣ ለተሰበሰበው ሰራዊት ቈጠራ ተደርጎ ነበር። ዕድሜ ያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ የነበሩት እነዚያ ከመጀመሪ ያው ትውልድ የተቈጠሩት ሰዎች ሁሉ ሞተዋል። ወደፊት ለሚጠብቀው ጦርነት ዝግጁ ለመሆን በዚህ ጊዜ አዲሱ ትው ልድ ተሰብስቦ መቈጠሩ እጅግ ያስፈልግ ነበር። በዚህ ወቅት አሮን ሞቶአል (20፥28 ይመ)፤ በዕድሜ የገፋው ሙሴም በሥራው እንዲያግዘው የወንድሙ ልጅ አልዓዛር ተመድቦለት ነበር። በዚህ ሁለተኛ ቈጠራ ውስጥ ዋና ዋና የሆኑት ነገዶች ተዘርዝረዋል። የአብዛኞቹ ነገዶች የሕዝብ ቍጥር ጨምሮአል። የሕዝብ ቍጥራ ቸው ከቀነሱት ነገዶች አንዱ የሮቤል ነገድ ነው። ቆሬና ከሮቤል ወገን የሆኑት ተባባሪዎቹ ባስነሡት ዐመፅ በሞት ስለ ተቀጡ (የቍ 9 ማብ ይመ)፣ በሮቤል ነገድ የሕዝብ ብዛት ላይ መጠነኛ የሆነ የማነስ ለውጥ የታየው በዚህ ምክንያት ሊሆን ይችላል። ከዚያ በኋላ በመካከል በነበሩት ዓመታት የሮቤል ነገድ ቍጥር ከመጀመሪያው ብዛት ጋር የተቀራረበ ነበር (የቍ 14 ማብ ይመ)። በመጀመሪያውና በሁለተኛው የሕዝብ ቈጠራ ጊዜ የተመ ዘገበው፣ በእያንዳንዱ ነገድ የተደረገው ንጽጽር ከዚህ እንደሚከ ተለው ነው፤

| ነገድ | የመጀመሪያው ቈጠራ | ሁለተኛው ቈጠራ |
|---|---|---|
| ሮቤል | 46,500 | 43,730 |
| ስምኦን | 59,300 | 22,200 |
| ጋድ | 45,650 | 40,500 |
| ይሁዳ | 74,600 | 76,500 |
| ይሳኮር | 54,400 | 64,300 |
| ዛብሎን | 57,400 | 60,500 |
| ኤፍሬም | 40,500 | 32,500 |
| ምናሴ | 32,200 | 52,700 |
| ብንያም | 35,400 | 45,600 |
| ዳን | 62,700 | 64,400 |
| አሴር | 41,500 | 53,400 |
| ንፍታሌም | 53,400 | 45,400 |
| ጠቅላላ ድምር | 603,550 | 601,730 |

[8]የፈሉስ ልጅ ኤልያብ ሲሆን፣ [9]የኤልያብ ልጆች ደግሞ፣ ነሙኤል ዳታንና አቤሮን ነበሩ። እነዚሁ ዳታንና አቤሮን በሙሴና በአሮን ላይ ያመፁ የማኅበሩ ሹማምንት ሲሆኑ፣ ቆሬና ተከታዮቹ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ላይ ባመፁ ጊዜ እነርሱም በነገሩ ነበሩበት። [10]ሁለት መቶ አምሳዎቹን ሰዎች እሳት በበላቻቸው ጊዜ የቆሬ ተከታዮች ሲሞቱ እነዚህን ደግሞ ምድር ተከፍታ ከእርሱ ጋር ዋጠቻቸው፤ መቀጣጫም ሆኑ፤ [11]የቆሬ የዘር ሐረግ ግን አልጠፋም።

[12]የስምዖን ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በነሙኤል በኩል፣ የነሙኤላውያን ጐሣ፤
በያሚን በኩል፣ የያሚናውያን ጐሣ፤
በያኪን በኩል፣ የያኪናውያን ጐሣ፤
[13]በዛራ በኩል፣ የዛራውያን ጐሣ፤
በሳኡል በኩል፣ የሳኡላውያን ጐሣ፤
[14]እነዚህ የስምዖን ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህ የተቈጠሩትም ሃያ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ነበሩ።

[15]የጋድ ዘሮች በየጐሣዎቻቸው እነዚህ ነበሩ፤
በጽፎን በኩል፣ የጽፎናውያን ጐሣ፤
በሐጊ በኩል፣ የሐጋውያን ጐሣ፤
በሹኒ በኩል፣ የሹናውያን ጐሣ፤
[16]በኤስና በኩል፣ የኤስናናውያን ጐሣ፤
በዔሪ በኩል፣ የዔራውያን ጐሣ፤
[17]በአሮዲ[†] በኩል፣ የአሮዳውያን ጐሣ፤
በአርኤሊ በኩል፣ የአርኤላውያን ጐሣ፤
[18]እነዚህ የጋድ ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከነዚህ የተቈጠሩት አርባ ሺህ አምስት መቶ ነበሩ።

[19]ዔርና አውናን የይሁዳ ልጆች ነበሩ፤ ነገር ግን በከነዓን ምድር ሞተዋል።
[20]የይሁዳ ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በሴሎም በኩል፣ የሴሎማውያን ጐሣ፤
በፋሬስ በኩል፣ የፋሬሳውያን ጐሣ፤
በዛራ በኩል፣ የዛራውያን ጐሣ፤
[21]የፋሬስ ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በኤስሮም በኩል፣ የኤስሮማውያን ጐሣ፤
በሐሙል በኩል፣ የሐሙላውያን ጐሣ፤
[22]እነዚህ የይሁዳ ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህ የተቈጠሩት ሰባ ስድስት ሺህ አምስት መቶ ነበሩ።

[23]የይሳኮር ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በቶላ በኩል፣ የቶላውያን ጐሣ፣
በፋዋ በኩል፣ የፋዋውያን ጐሣ፣
[24]በያሱብ በኩል፣ የያሱባውያን ጐሣ፣
በሺምሮን በኩል፣ የሺምሮናውያን ጐሣ፤
[25]እነዚህ የይሳኮር ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህ የተቈጠሩት ሥልሳ አራት ሺህ ሦስት መቶ ነበሩ።

[26]የዛብሎን ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በሴሬድ በኩል፣ የሴሬዳውያን ጐሣ፤
በኤሎን በኩል፣ የኤሎናውያን ጐሣ፣
በያሕልኤል በኩል፣ የያሕልኤላውያን ጐሣ፤
[27]እነዚህ የዛብሎን ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህ የተቈጠሩት ሥልሳ ሺህ አምስት መቶ ነበሩ።

[28]የዮሴፍ ዘሮች በምናሴና በኤፍሬም በኩል ያሉት በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
[29]የምናሴ ዘሮች፤
በማኪር በኩል፣ የማኪራውያን ጐሣ፤
ማኪርም የገለዓድ አባት ነው፤
በገለዓድ በኩል፣ የገለዓዳውያን ጐሣ፤
[30]የገለዓድ ዘሮች እነዚህ ነበሩ፤
በኢዔዝር በኩል፣ የኢዓዝራውያን ጐሣ፣
በኬሌግ በኩል፣ የኬሌጋውያን ጐሣ፣
[31]በአሥሪኤል በኩል፣ የአሥሪኤላውያን ጐሣ፣
በሴኬም በኩል፣ የሴኬማውያን ጐሣ፣
[32]በሸሚዳ በኩል፣ የሸሚዳውያን ጐሣ፣
በኦፌር በኩል፣ የኦፌራውያን ጐሣ፣
[33]የኦፌር ልጅ ሰለጰዓድ ወንዶች ልጆች አልነበሩትም፤ ልጆቹ ሴቶች ብቻ ነበሩ፤ እነርሱም ማህለህ፣ ኑዓ፣ ዔግላ፣ ሚልካና ቴርጻ ይባላሉ።
[34]እነዚህ የምናሴ ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህ የተቈጠሩት አምሳ ሁለት ሺህ ሰባት መቶ ነበሩ።

[35]የኤፍሬም ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በሱቱላ በኩል፣ የሱቱላውያን ጐሣ፣
በቤኬር በኩል፣ የቤኬራውያን ጐሣ፣
በታሐን በኩል፣ የታሐናውያን ጐሣ፤
[36]የሱቱላ ዘሮች እነዚህ ነበሩ፤
በዔዴን በኩል፣ የዔዴውናውያን ጐሣ፤

[†]17 በአራተ ሳምራውያኑ ትጅ አሮዲ፣ በማሶሬቲክ ትጅ አሮድ ተብሎአል።

26፥9 ዘኍ 10፥16፤ 16፥1፡2
26፥10 ዘፀ 3፥12፤ 15፥12፤ ዘኍ 16፥35፡ 38
26፥11 ዘፀ 6፥24፤ ዘኍ 16፥33፤ ዘዳ 5፥9፤2 4፥16፤ 2ነገ 14፥6፤ 2ዜና 25፥4፤ ሕዝ 18፥20
26፥12 ዘፍ 46፥10፤ 1ዜና 4፥24
26፥13 ዘፍ 46፥10
26፥14 ዘፍ 46፥10፤ ዘኍ 1፥23
26፥15 ዘፍ 46፥16
26፥18 ዘፍ 30፥11፤ ዘኍ 1፥25፤ ኢያሱ 13፥24-28
26፥19 ዘፍ 38፥3፡ 4፡7
26፥20 ዘፍ 38፥5፡ 29፤ ኢያሱ 7፥17
26፥21 ዘፍ 38፥29፤ ሩት 4፥19፤ 1ዜና 2፥9
26፥22 ዘኍ 1፥27
26፥23 ዘፍ 46፥13
26፥24 ዘፍ 46፥13
26፥25 ዘፍ 30፥18
26፥26 ዘኍ 1፥30
26፥27 ዘፍ 30፥20
26፥28 ዘፍ 41፥52፤ ዘኍ 1፥32፤ 36፥1
26፥29 ዘፍ 50፥23፤ ዘኍ 1፥34፤ መሳ 11፥1
26፥30 ዘኍ 27፥1፤ 36፥1፤ ኢያሱ 17፥2፤ መሳ 6፥11፤ 8፥2፤ 1ዜና 7፥14፡17
26፥33 ዘኍ 27፥1፤ 3፤ 36፥2፤ 11፤ ኢያሱ 17፥3፤ 1ዜና 7፥15
26፥34 ዘኍ 1፥35
26፥35 ዘኍ 1፥32

26፥9 *ዳታንና አቤሮን*፤ የሮቤል ቤተ ሰብ መዘርዘሩ ከቤተ ሰቡ የተወሰኑ ሰዎች በቆሬ ዐመፅ መካፈላቸውን ይህን ክፍል ለሚያነብ ሰው የሚያስታውስ ነው (16፥1 ይመ፤ ከይሁዳ ቍ 11 ጋር ያነጻጽሩ)።

26፥14 *ሃያ ሁለት ሺህ ሁለት መቶ*፤ ከአምሳ ዘጠኝ ሺህ ሦስት መቶ ሰዎች የተረፉት ቍጥር ሲታይ፣ ከስምዖን ነገድ የሞተው ሰው ብዛት እጅግ ከፍተኛ መሆኑን ያመለክታል። ዘንበሪ ከስምዖን ቤት ነበር (25፥14)። በእልን በማምለካቸው በእግዚአብሔር መቅሠፍት ከሞቱት ሃያ አራት ሺህ ሰዎች ውስጥ አብዛኞቹ ከስምኦን ነገድ ሊሆኑ ይችላሉ። ፍርዱ የሆነው በቅርብ ስለነበር፣ የስምኦን ነገድ እንደ ሮቤል ነገድ (የቍ 1-51 ማብ ይመ) በቂ ጊዜ አግኝቶ ቍጥሩ ሊጨምር አልቻለም።

26፥19 *ዔርና አውናን*፤ የይሁዳ ክፉ ልጆች ስማቸው ሳይረሳ ተጠቅሶአል፤ ነገር ግን የውርስ ድርሻ አልነበራቸውም (ዘፍ 38፥1-10 ይመ)

26፥20 *ፋሬስ*፤ የዳዊትና የኢየሱስ የትውልድ ሐረግ ከዚህ ሰው ዘር ተያይዞ የመጣ ነው (ሩት 4፥18-22፤ ማቴ 1፥1-3)።

26፥29፡35 *ምናሴ … ኤፍሬም*፤ የኤፍሬምና የምናሴ ነገድ ስም ዝርዝር አጻጻፉ ተቀያየረ እንጂ የነገዶቹ ቅደም ተከተል በምዕራፍ አንድ ላይ ተዘርዝሮ እንደ ተጻፈው ነው።

26፥33 *የሰለጰዓድ … ሴቶች ልጆች*፤ 27፥1-11፤ 36 ይመ።

26፥34 *አምሳ ሁለት ሺህ ሰባት መቶ*፤ ከሁሉም ይልቅ ቍጥሩ የጨመረው የምናሴ ነገድ ነበር፤ ቀደም ሲል በነገዱ ሥር የተመዘገበው ሠላሳ ሁለት ሺህ ነበር፣ ይሁን እንጂ ለቍጥሩ መጨመር ምክንያት የሆነው ነገር አልተገለጸም።

[37]እነዚህ የኤፍሬም ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነ ዚህ የተቈጠሩት ሠላሳ ሁለት ሺህ አምስት መቶ ነበሩ።
እነዚህም በየጐሣቸው የተቈጠሩ የዮሴፍ ዘሮች ነበሩ።

[38]የብንያም ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በቤላ በኩል፣ የቤላውያን ጐሣ፣
በአስቤል በኩል፣ የአስቤላውያን ጐሣ፣
በአኪራን በኩል፣ የአኪራናውያን ጐሣ፣
[39]በሶፋን[1] በኩል፣ የሶፋናውያን ጐሣ፣
በሑፋም በኩል፣ የሑፋማውያን ጐሣ፤
[40]የቤላ ዘሮች በአርድና በናዕማን በኩል፤
በአርድ በኩል፣ የአርዳውያን ጐሣ፣
በናዕማን በኩል፣ የናዕማናውያን ጐሣ፤
[41]እነዚህ የብንያም ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚ ህም የተቈጠሩት አርባ አምስት ሺህ ስድ ስት መቶ ነበሩ።

[42]የዳን ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በሰምዔ በኩል፣ የሰምዔያውያን ጐሣ ዎች።
እነዚህ እንግዲህ የዳን ጐሣዎች ሲሆኑ፣
[43]ሁሉም የሰምዔያውያን ጐሣዎች ነበሩ፤ ከእነዚህ የተቈጠሩት ደግሞ ሥልሳ አራት ሺህ አራት መቶ ነበሩ።

[44]የአሴር ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በዪምና በኩል፣ የዪምናውያን ጐሣ፣
በየሱዋ በኩል፣ የየሱዋውያን ጐሣ፣
በበሪዓ በኩል፣ የበሪዓውያን ጐሣ፤
[45]እንዲሁም በበሪዓ ዘሮች በኩል፣
በሐቤር በኩል፣ የሐቤራውያን ጐሣ፣
በመልኪኤል በኩል፣ የመልኪኤላው ያን ጐሣ።
[46]አሴር ሤራሕ የምትባል ልጅ ነበረ ችው።
[47]እነዚህ የአሴር ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእነዚህ የተቈጠሩት አምሳ ሦስት ሺህ አራት መቶ ነበሩ።

[48]የንፍታሌም ዘሮች በየጐሣቸው እነዚህ ነበሩ፤
በያሕጽኤል በኩል፣ የያሕጽኤላውያን ጐሣ፣
በጉኒ በኩል፣ የጉናውያን ጐሣ፣
[49]በሺሌም በኩል፣ የሺሌማውያን ጐሣ፤
[50]እነዚህ የንፍታሌም ጐሣዎች ሲሆኑ፣ ከእ ነዚህ የተቈጠሩት አርባ አምስት ሺህ አራት መቶ ነበሩ።
[51]ባጠቃላይ የእስራኤል ወንዶች ቍጥር ስድስት መቶ አንድ ሺህ ሰባት መቶ ሠላሳ ነበር።

26፥37 ዘኍ1፥33
26፥38 ዘፍ46፥21፤ ዘኍ1፥36፤1ዜና8፥40
26፥40 ዘፍ46፥21
26፥41 ዘኍ1፥37
26፥42 ዘፍ46፥23፤ ዘኍ1፥38፤መሳ18፥19
26፥44 ዘኍ1፥40
26፥47 ዘኍ1፥41
26፥48 ዘፍ30፥8
26፥50 ዘኍ1፥42፡ 43
26፥51 ዘፀ12፥37
26፥53 ቍ55፤ኢሱ 11፥23፤14፥1፤ሕዝ 45፥8
26፥54 ዘኍ33፥ 54፤35፥8
26፥55 ዘሌ16፥8
26፥57 ዘፍ46፥11
26፥58 ዘፀ6፥20
26፥59 ዘፀ2፥1፡4፤ 6፥20፤15፥20
26፥60 ዘፀ6፥23
26፥61 ዘሌ10፥1-2 ዘኍ3፥4
26፥62 ዘኍ1፥47፤ 2፥33፤3፥39፤18፥23
26፥63 ቍ3፤ዘኍ 1፥19፤22፥1
26፥64 ዘኍ1፥44፤ 14፥29

[52]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [53]"ምድሪቱ በስማቸው ቍጥር ልክ ተደልድላ በርስትነት ለእነርሱ ትሰጥ። [54]በር ከት ያለ ቍጥር ላለው ጐሣ ሰፋ ያለውን ርስት፣ አነስ ያለ ቍጥር ላለው ጐሣ ደግሞ አነስ ያለውን ስጥ፤ ርስቱንም እያንዳንዱ በዝርዝሩ ላይ በተመለከተው ቍጥር መሠ ረት ይረከባል። [55]የመሬት ድልድሉም በዕጣ ይሁን፤ እያንዳንዱ የሚወርሰውም በየነገድ አባቶቹ ስም ይሆናል። [56]እያንዳንዱም ርስት በትልልቆቹና በትንንሾቹ ነገዶች መካከል በዕጣ ይደለደላል።

[57]በየጐሣቸው የተቈጠሩት ሌዋውያን እነዚህ ነበሩ፤
በጌድሶን በኩል፣ የጌድሶናውያን ጐሣ፣
በቀዓት በኩል፣ የቀዓታውያን ጐሣ፣
በሜራሪ በኩል፣ የሜራራውያን ጐሣ፤
[58]እነዚህም ደግሞ የሌዊ ጐሣዎች ነበሩ፤
የሊብናውያን ጐሣ፣
የኬብሮናውያን ጐሣ፣
የሞሖላውያን ጐሣ፣
የሙሳውያን ጐሣ፣
የቆሬያውያን ጐሣ።
ቀዓት የእንበረም ቅድመ አያት ነበር፤ [59]ሚስቱ ዮካብድ ትባል ነበር፤ እርሷም በግብፅ አገር ከሌዋውያን የተወለደች የሌዊ ዘር ነበረች። ከእንበረምም አሮ ንን፣ ሙሴንና እኅታቸውን ማርያምን ወለደች። [60]አሮንም የናዳብና የአብዩድ፣ የአልዓዛርና የኢታምር አባት ነበር። [61]ነገር ግን ናድብና አብዩድ ባልተፈ ቀደ እሳት ለእግዚአብሔር (ያህዌ) መሥ ዋዕት ስላቀረቡ ሞቱ።

[62]አንድ ወርና ከዚያ በላይ የሆናቸው ሌዋውያን ወንዶች ሁሉ ተቈጥረው ሃያ ሦስት ሺህ ሆኑ፤ እነርሱም ከሌሎቹ እስራ ኤላውያን ጋር ርስት ተካፋዮች ስላልነበሩ አብረዋቸው አልተቈጠሩም።
[63]ሙሴና ካህኑ አልዓዛር ከኢያሪኮ ማዶ በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ ካለው ከሞዓብ ሜዳ ላይ የእስራኤልን ሕዝብ በቈጠሩበት ወቅት የተቈጠሩት እነዚህ ናቸው። [64]ሙሴና ካህኑ አሮን በሲና ምድረ በዳ እስራኤላው ያንን በቈጠሩ ጊዜ ከእነዚህ ከተቈጠሩት መካከል አንዳቸውም አልነበሩም፤ [65]ምክን ያቱም በእርግጥ በምድረ በዳ እንደሚሞቱ

[1]39 ጥቂት የማሶሬቲክ፣ የአሪተ ሳምራውያን፣ የቩልጌትና የሱር ስት ቅጆች ሰፋን የሚሉ ሲሆን፣ አያሌ የማሶሬቲክ ቅጆች ግን ሼፉፋም ይላሉ።

26፥46 *ሤራሕ የምትባል ልጅ፣* የዚህች ሴት ልጅ ስም በተለይ መጠቀሱ የሚያስገርም ነው።
26፥51 *ስድስት መቶ አንድ ሺህ ሰባት መቶ ሠላሳ፣* ሕዝቡ ሁሉ በምድረ በዳው ጉዞ ወቅት ባጋጠመው ችግርና ውጣ ውረድ ከመጀመሪያ አንሥቶ እስከ መጨረሻ የነበረ ቢሆንም፣ ጠቅላላ ቍጥሩ ግን ከመጀመሪያው ብዙም የተራራቀ አልነበረም። እግዚ አብሔር የገባውን ብዙ ኪዳን ለመፈጸም በያዕቆብ በኩል የአብ ርሃም ትውልድ የሆነውን ሕዝብ (ዘፍ 12፥2-3) ቍጥሩ እንዲበዛ ያደረገ ሲሆን፣ ይህ አስደናቂ ነገር የእግዚአብሔር በረከት እንደ ሆነ መቈጠር አለበት። ይህ ጠቅላላ ድምርና በሥሩ የተዘረዘረው የእያንዳንዱ ነገድ ብዛት፣ በመጽሐፉ ውስጥ ከተጠቀሰው አጠቃ ላይ ቍጥር ጋር የተስማማ ነው (የ1፥46 ማብ ይመ)።
26፥53 *በስማቸው ቍጥር ልክ ተደልድላ፤* ከፍተኛ ቍጥር ያለው ነገድ ሰፋ ያለ መሬት የሚሰጠው ሲሆን፣ የቦታው ምርጫ ግን በዕጣ ይወሰናል (ቍ 55)።
26፥57 *ሌዋውያን፣* በመጀመሪያው ቈጠራ ላይ እንደተደ ረገው ሁሉ (ም 3) በሁለተኛውም ቈጠራ ሌዋውያን በተለይ ተቈጥረዋል።

ያን ጊዜ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነግሮአቸው ነበር፣ ከዮፎኒ ልጅ ከካሌብና ከነዌ ልጅ ከኢያሱ በስተቀር ከእነርሱ የተረፈ ማንም ሰው አልነበረም።

## የሰለጰዓድ ሴት ልጆች

**27** የምናሴ ልጅ፣ የማኪር ልጅ፣ የገለዓድ ልጅ፣ የኦፌር ልጅ፣ የሰለጰዓድ ሴት ልጆች ከዮሴፍ ልጅ ከምናሴ ጐሣዎች ነበሩ፤ ስማቸውም ማህለህ፣ ኑዓ፣ ዔግላ፣ ሚልካና ቲርጻ ይባላል። እነርሱም፣ [2]ወደ መገናኛው ድንኳን መግቢያ ቀረቡ፤ በሙሴ፣ በካህኑ በአልዓዛር፣ በመሪዎችና በመላው ማኅበርም ፊት ቆመው እንዲህ አሉ፤ [3]"አባታችን በምድረ በዳ ሞተ፤ ተባብረው *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ላይ ካመፁት ከቆሬ ተከታዮች ጋር አልነበረም፤ የሞተው ግን በራሱ ኀጢአት ሲሆን፣ ወንዶች ልጆችም አልነበሩትም። [4]ታዲያ አባታችን ወንድ ልጅ ባለመውለዱ ስሙ ከጐሣዎቹ ተለይቶ እንዴት ይጠፋል? ለእኛም በአባታችን ዘመዶች መካከል ርስት ስጡን።"

[5]ስለዚህ ሙሴ ጕዳያቸውን ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) አቀረበ፤ [6]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) እንዲህ አለው፤ [7]"የሰለጰዓድ ልጆች ጥያቄ ትክክል ነው፤ በእርግጥ በአባታቸው ዘመዶች መካከል ድርሻቸውን ርስት አድርገህ ልትሰጣቸው ስለሚገባ የአባታቸውን ድርሻ ለእነርሱ አስተላልፍላቸው።

[8]"እስራኤላውያንን እንዲህ በላቸው፤ 'አንድ ሰው ወንድ ልጅ ሳይተካ ቢሞት ውርሱን ለሴት ልጁ አስተላልፉ። [9]ሴት ልጅ ከሌለችው ደግሞ ውርሱን ለወንድሞቹ ስጡ። [10]ወንድሞች ከሌሉትም ውርሱን ለአባቱ ወንድሞች ስጡ። [11]አባቱ ወንድሞች ከሌሉት ውርሱ ከጐሣው መካከል ቅርብ ለሆነ ዘመዱ ይሰጥ፤ እርሱም ይውረሰው። ይህም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ለእስራኤላውያን ሕጋዊ መመሪያ ይሆናቸዋል።'"

## ኢያሱ በሙሴ እግር ተተካ

[12]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "በዓባሪም ሸንተረር ላይ ወዳለው ወደዚህ ተራራ ውጣና ለእስራኤላውያን የሰጠኋቸውን ምድር እይ። [13]ካየኸውም በኋላ አንተም እንደ ወንድምህ እንደ አሮን ወደ ሕዝብህ ትሰበሰባለህ፤ [14]ምክንያቱም ማኅበረ ሰቡ በጺን ምድረ በዳ ባለው ውሃ አጠገብ ባመፁ ጊዜ እኔን በሕዝቡ ፊት ቅዱስ አድርጋችሁ ለማክበር ሁለታችሁም ትእዛዜን ስላልጠበቃችሁ ነው።" ይህም በጺን ምድረ በዳ በቃዴስ የሚገኝ የመሪባ ውሃ ነው።

[15]ሙሴ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዲህ አለው፤ [16]"የሰብአዊ ፍጡር ሁሉ መንፈስ ስምዓክ (ኤሉሂም) የሆነ ጌታ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በዚህ ማኅበረ ሰብ ላይ ሰው ይሹም፤ [17]እርሱም፣ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ሕዝብ እረኛ እንደሌለው የበግ መንጋ እንዳይሆን በፊቱ የሚወጣና የሚገባ፣ መርቶ የሚያወጣውና የሚያገባው እንዲሆን ነው።"

[18]ስለዚህም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ "መንፈስ ቅዱስ[1] ያደረበትን የነዌን ልጅ ኢያሱን ወስደህ እጅህን ጫንበት። [19]በካህኑ በአልዓዛርና በመላው ማኅበር ፊት እንዲቆም አድርገው፤ በፊታቸውም ሹመው፤ [20]መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ እንዲታዘዝለትም ከሥልጣንህ ከፍለህ ስጠው። [21]እርሱም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ሆኖ በኡሪም በመጠየቅ ውሳኔ በሚያስገኝለት በካህኑ በአልዓዛር ፊት ይቆማል፤ እርሱም ሆነ መላው የእስራኤል ማኅበረ ሰብ በአልዓዛር ትእዛዝ ይወጣሉ፤ በእርሱም ቃል ይገባሉ።"

[22]ሙሴም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዳዘዘው አደረገ፤ ኢያሱንም ወስዶ በካህኑ በአልዓዛርና በመላው የእስራኤል ማኅበር ፊት አቆመው፤

[1]18 *ወይም መንፈስ*

26፥65 ዘኍ14፥28፤13፥6፤14፥28፤ 1ቆሮ10፥5
27፥1 ዘፍ50፥23፤ ዘኍ26፥30፡33፤ኢሱ 17፥2፡3፤1ዜና2፥21
27፥2 ዘፀ40፥2፡ 17፤ዘኍ1፥16፤9፥6፤ 31፥13፤32፥2፤36፥1
27፥3 ዘኍ16፥2፤ 26፥33፡65
27፥5 ዘፍ25፥22፤ዘፀ 18፥19፤ዘኍ9፥8
27፥7 ቍ8፤ኢሱ 17፥4፤ኢዮ42፥15
27፥11 ዘኍ35፥29
27፥12 ዘኍ23፥14፤ 33፥47፤ዘሌ14፥34፤ ዘዳ3፥23-27፤32፥ 48-52፤ኤር22፥20
27፥13 ዘኍ20፥12፡ 28፤31፥2፤ዘዳ4፥22፤ 31፥14፤32፥50፤ 1ነገ2፥1
27፥14 ዘፀ17፥7፤ ዘኍ20፥1፡2-5፡12
27፥16 ዘኍ16፥22፤ ኢዮ21፥20
27፥17 1ነገ22፥17፤ 2ዜና18፥16፤ሕዝ 34፥5፤ዘካ10፥2፤ ማቴ9፥36
27፥18 ቍ23፤ዘፍ 41፥38፤ዘኍ11፥25- 29፤ዘዳ34፥9፤ሐሥ 6፥6
27፥19 ቍ23፤ዘዳ 3፥28፤31፥7፡14፡23
27፥20 ኢሱ1፥16፡17
27፥21 ዘፍ25፥22፤ ዘፀ28፥30፤ኢሱ9፥14፤ መዝ106፥13፤ኢሳ8፥ 19፤ሐጌ1፥13፤ሚል 2፥7፤3፥1

*27፥1-11፤* ወንድ ልጅ ሳይወልድ የሞተው ሰው፣ ሴት ልጆቹ (26፥33 ይመ) የመውረስ መብታቸውን ለማስከበርና የአባታቸውን ስም በምድሪቱ ለማስጠራት (ቍ 4) ተቈርቍረው ተነሡ። ሴቶቹ ወደ ሙሴና አልዓዛር፣ ወደ ሕዝቡም አለቆች ዘንድ ቀርበው ያደረጉት ነገር ያልተለመደና በጽኑነት ድፍረትን የተሞላ ነበር።

27፥3 *የሞተው ግን በራሱ ኀጢአት ሲሆን፤* በምድረ በዳ ያለቁት ሰዎች (26፥64-65 ይመ) ከሞቱበት ኀጢአት የተለየ ነው። በእምነታቸው ጽኑ አቋም የያዙ እነዚህ ሴቶች፣ ስለ ምድረ በዳው ጕዞ በቂ ግንዛቤ ነበራቸው፤ ስለ ቤተ ሰባቸውም ፍትሐዊ ጥያቄ አቀረቡ።

27፥4 *ርስት ስጡን፤* አንድ ሰው ወንዶች ልጆች ከሌሉት ይዞታው ለሌላ እንዳይተላለፍ በዕብራይስጥ ሕግ የተከለከለ ነበር፤ ነገር ግን እግዚአብሔር፣ ሴት ልጅ ከአባቷ የመሬት ይዞታና የቤተ ሰቧን ድርሻ እንድትወርስ የሚያደርግ ሕግ ሰጠ።

27፥5 *ሙሴ ጕዳያቸውን ወደ እግዚአብሔር አቀረበ፤* ለየት ያለ ጕዳይን የሚመለከት ሕግ በእስራኤል ዘንድ እንዴት ተግባራዊ ይሆን እንደ ነበር ይህ ቍጥር በግልጽ ያሳያል። መሠረታዊ የሆኑ መመሪያ ሕጎች ይታወቁ ነበር። በሕጉ ውስጥ የሌሉ ተገቢ የሆኑ ጥያቄዎችና የተለዩ ሐሳቦች ለሕዝቡ አለቆች ምናልባትም ለሙሴ ለራሱ ይቀርቡ እንደ ነበር፣ እርሱም ለቀረበው ጕዳይ ውሳኔውን ከእግዚአብሔር ይጠብቅ ነበር። በዚህ ጕዳይ ላይ እግዚአብሔር ለእነዚህ ሴቶች የሚስማማ ውሳኔ ሰጠ። ይህን በሚመለከት በም 36 ላይ ተጨማሪ ሐሳብ ተሰጥቶአል።

*27፥12-23፤* የሰለጰዓድ ሴት ልጆች የአባታቸውን መሬት ለመውረስ (ቍ 1-11) ጥያቄ የማቅረባቸው ሁኔታ፣ ሙሴ ከመሬቱ ድርሻ እንዳይኖረው (ቍ 12-14) እግዚአብሔር ካደረገው ነገር ጋር ሲነጻጸር የሚያሳዝን ነው። በውርስ ሕጉ ውስጥ ላልተካተቱና ከተለመደው አሠራር ውጭ ለሚያጋጥሙ ጕዳዮች አስፈላጊውን ነገር የሚያደርግ ቢሆንም፣ ሙሴ ምንም ያገኘው ድርሻ አልነበረም። ሙሴ፣ በቃዴስ በመሪባ ውሃ አጠገብ የሠራው ኀጢአት (20፥1-13) ሁል ጊዜ ይታወስ ነበር።

27፥16 *ሰው ይሹም፤* ሙሴ በያዘው የመሪነት ስፍራ እንደማይቀጥል ሲነገረው የሰጠው ምላሽ በምትኩ ስለሚሾመው ሰው መጸለይ ነበር።

27፥18 *ኢያሱን ወስደህ፤* አሮን ከመሞቱ በፊት ሙሴና አሮን አንድ ላይ ሆነው የሚተካውን ሰው መወሰን እንደነበረባቸው ሁሉ (20፥22-29)፣ ሙሴንም የሚተካ ትክክለኛውን ሰው መሾም አስፈላጊ ነበር። እስራኤል እምነቷን ጥላ ሁሉም ነገር ጨለማ በሆነባት ሰዓት ሁለቱ የእምነት ጀግኖች ኢያሱና ካሌብ ነበሩ (ም 13-14)። እግዚአብሔር ከሁለቱ አንዳቸውን መምረጡ ተገቢ ነበር (ከዘፀ 17፥9-14፤ 24፥13፤ 32፥17፤ 33፥11 ጋር ያነጻጽሩ)።

27፥20 *ከሥልጣንህ ከፍለህ ስጠው፤* ከሙሴ አመራር በኋላ፣ የመሪነቱን ሥልጣን ወደሚተካው ሰው ማሸጋገር አስቸጋሪ ነበር። ሙሴ በሕይወት እያለ ቀስ በቀስ ሥልጣኑን ለሚተካው ሰው በማስተላለፍ፣ ለውጡን በተረጋጋ ሁኔታ ማሸጋገር ይገባ ነበር።

[23]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) በሙሴ አማካ ይነት ባዘዘው መሠረት እጁን በራሱ ላይ ጭኖ ሾመው::

## የየዕለቱ መሥዋዕት

**28** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2]"ይህን ትእዛዝ ለእስራኤላውያን ስጣቸው፤ 'ሽታው ደስ እንዲያሰኘኝ በእሳት የሚቀርብልኝን የምግብ ቍርባን የተወሰነውን ጊዜ ጠብቃችሁ አቅርቡልኝ' በላቸው:: [3]ደግሞም እንዲህ በላቸው፤ 'በእሳት ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የምታቀርቡት መሥዋዕት ይህ ነው፤ አንድ ዓመት የሆናቸውና እንከን የሌለባቸውን ሁለት ተባዕት የበግ ጠቦቶች መደበኛ የሚቃጠል መሥዋዕት በማድረግ በየዕለቱ አቅርቡ:: [4]አንዱን ጠቦት ጠዋት ሌላውን ደግሞ ማታ አቅርቡ፤ [5]ከዚህም ጋር ተወቅጦ በተጠለለ በሂን[ሀ] አንድ አራተኛ የወይራ ዘይት የተለወሰ የኢፍ[ለ] አንድ ዐሥረኛ ልም ዱቄት የእህል ቍርባን አዘጋጁ:: [6]ይህም ሽታው ደስ እንዲያሰኝ በእሳት ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የሚቀርብ ምሥዋዕት ሲሆን፣ በሲና ተራራ የተደነገገ መደበኛ የሚቃጠል መሥዋዕት ነው:: [7]ከእያንዳንዱ ጠቦት ጋር አብሮት የሚቀርበውም የመጠጥ ቍርባን ፈልቶ የወጣለት የሂን አንድ አራተኛ መጠጥ ይሆናል፤ የመጠጡንም ቍርባን በተቀደሰው ቦታ ላይ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) አፍስሱት:: [8]ሁለተኛውንም ጠቦት ጠዋት ባቀረባችሁት ዐይነት አድርጋችሁ ከእህል ቍርባኑና ከመጠጥ ቍርባኑ ጋር ማታ አቅርቡት፤ ይህም ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ በእሳት የሚቀርብ መሥዋዕት ነው::

## የሰንበት መሥዋዕት

[9]" 'በሰንበት ዕለት፣ አንድ ዓመት የሆናቸውንና እንከን የማይገኝባቸውን ሁለት ተባዕት የበግ ጠቦቶች መሥዋዕት ከመጠጥ ቍርባኑና በዘይት ከተለወሰ የኢፍ[ሐ] ሁለት ዐሥረኛ ልም ዱቄት ጋር አቅርቡ:: [10]ይህም ከመጠጥ ቍርባኑ ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ በየሰንበቱ የሚቀርብ የሚቃጠል መሥዋዕት ነው::

## የየወሩ መሥዋዕት

[11]" 'በየወሩ መባቻ እንከን የሌለባቸውን ሁለት ወይፈኖች፣ አንድ አውራ በግ፣ ዓመት የሆናቸውን ሰባት ተባዕት የበግ ጠቦቶችን የሚቃጠል መሥዋዕት አድርጋችሁ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) አቅርቡ:: [12]ከእያንዳንዱ ወይፈን ጋር ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ የኢፍ[መ] ሦስት ዐሥረኛ ልም ዱቄት፣ ከአውራውም በግ ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ የኢፍ ሁለት ዐሥረኛ ልም ዱቄት ይቀርባል፤ [13]እንደዚሁም ከእያንዳንዱ የበግ ጠቦት ጋር ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ የኢፍ አንድ ዐሥረኛ ልም ዱቄት አቅርቡ፤ ይህም ለሚቃጠል መሥዋዕት ሲሆን ሽታው ደስ የሚያሰኝና በእሳት ለእግዚአብሔር (ያህዌ) የሚቀርብ መሥዋዕት ነው:: [14]ከእያንዳንዱ ወይፈን ጋር ለመጠጥ ቍርባን የሚሆን የኢን[ሠ] ግማሽ የወይን ጠጅ፣ ከአውራው በግ ጋር የኢን[ረ] አንድ ሦስተኛ፣ ከእያንዳንዱም የበግ ጠቦት ጋር የኢን አንድ አራተኛ የወይን ጠጅ ይቀረብ፤ ይህም በየወሩ መባቻ ዓመቱን ሙሉ የሚቀርብ የሚቃጠል መሥዋዕት ነው:: [15]ከመጠጥ ቍርባኑ ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት ሆኖ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ይቀርባል::

## ፋሲካ

28፥16-25 ተጓ ምብ - ዘፀ 12፥14-20፤ ዘሌ 23፥4-8፤ ዘዳ 16፥1-8

[16]" 'የመጀመሪያው ወር በገባ በዐሥራ አራተኛው ቀን የእግዚአብሔር (ያህዌ) ፋሲካ በዓል ይከበራል:: [17]በዚሁ ወር በዐሥራ አምስተኛው ቀን በዓል ይሆናል፤ እስከ ሰባትም ቀን ድረስ ያለ እርሾ የተጋገረ ቂጣ ብሉ:: [18]በመጀመሪያው ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ የዘወትር ተግባራችሁንም አትሥሩበት:: [19]እንከን የሌለባቸው ሁለት ወይፈኖች፣ አንድ አውራ በግና ዓመት የሆናቸው ሰባት ተባዕት የበግ ጠቦቶች በእሳት የሚቃጠል መሥዋዕት በማድረግ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) አቅርቡ:: [20]ከእያንዳንዱም ወይፈን ጋር ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ የኢፍ ሦስት ዐሥረኛ ልም ዱቄት፣ ከአውራውም በግ ጋር የኢፍ ሁለት ዐሥረኛ ልም ዱቄት አቅርቡ፤ [21]ከሰባቱም የበግ ጠቦቶች ከእያንዳንዳቸው ጋር የኢፍ አንድ ዐሥረኛ ልም ዱቄት አዘጋጁ:: [22]በተጨማሪም ማስተስረያ እንዲሆናችሁ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ አቅርቡ:: [23]እነዚህንም ጧት ጧት በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ጋር አቅርቧቸው:: [24]በዚህም ዐይነት ሽታው እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ ሆኖ በየዕለቱ

27፥23 ቍ19
28፥2 1፥9፤3፥11፤ ዘሌ23፥1-44
28፥3 ዘፀ12፥5፤ 29፥38፤አሞ4፥4
28፥4 ዘፀ29፥39
28፥5 ዘሌ2፥1፤ 6፥20፤ዘኍ29፥6
28፥6 ዘፀ19፥3፤ ዘሌ1፥3:9
28፥7 ዘሌ3፥7፤ 10፥9፤23፥13፤ዘኍ 3፥28፤6፥15
28፥8 ቍ2፤ዘፀ 29፥39፤ዘሌ1፥9፤3፥7
28፥9 ቍ3:5፤ዘፀ 20፥10፤ዘሌ23፥13 ማቴ12፥5
28፥10 ቍ3፤ ዘሌ23፥38
28፥11 ዘሌ1፥3፤ 5፥15፤ዘኍ7፥15፤ 10፥10
28፥12 ቍ20፤ዘኍ 15፥6:9፤29፥3
28፥13 ቍ21፤ዘሌ 1፥9፤6፥14፤ዘኍ15፥3
28፥14 ቍ11፤ዘኍ 15፥7፤2ዜና2፥4፤ዕዝ 3፥5
28፥15 ቍ3:23: 24:30፤ዘሌ4፥3፤ዘኍ 29፥16:19
28፥16 ዘፀ12፥11፤ 2ዜና30፥13፤35፥1
28፥17 ዘፀ12፥15: 19
28፥18 ዘፀ12፥16
28፥19 ቍ11፤ ዘሌ1፥9
28፥20 ቍ12፤ ዘሌ14፥10
28፥21 ቍ13
28፥22 ዘሌ4፥3፤ ዘኍ15፥28ሮሜ8፥3
28፥24 ዘሌ1፥9

[ሀ]5 አንድ ሊትር ያህል ነው:: [ለ]5 ሁለት ሊትር ያህል ነው::
[ሐ]9 አራት ተኩል ሊትር ያህል ነው::
[መ]12 ስድስት ተኩል ሊትር ያህል ነው::
[ሠ]14 ሁለት ሊትር ያህል ነው:: [ረ]14 አንድ ሊትር ያህል ነው::

*28፥1-29፥40፤* በእነዚህ ምዕራፎች መሥዋዕት ማቅረብ በሰዎች ሕይወት ውስጥ ያለውን ከፍተኛ ስፍራና የካህናት ኀላፊነት ምን ያህል ሰፊ እንደ ሆነ ተገልጿል:: እነዚህ የመጽሐፉ ክፍሎች በዚህ ጊዜ መጻፋቸው በቅርብ ጊዜ ከሚሆነው የሥልጣን ሽግግር ማለት ከሙሴ ወደ ኢያሱ የመሪነት ሥልጣን መተላለፍ ጋር ለማያያዝ ይሆናል (27፥12-23)::

*28፥1-8፤* ዘፀ 29፥38-41፤ ዘሌ 1-7 እና ማብ ይመ::

*28፥9-10፤* ዘወትር ከሚደረገው መሥዋዕት ሌላ በሰንበት ቀን የተለየ መሥዋዕት ይቀርብ ነበር::

*28፥11-15፤* በወሩ መጀመሪያ ላይ የሚቀርቡ መሥዋዕቶች እጅግ አስፈላጊ ነበሩ፤ ይህም በዓል በሚደረግበትና ለአምልኮ መለከቶች በሚነፉበት ጊዜ ነበር (10፥10 ይመ)::

*28፥16-25፤* በዓመቱ መጀመሪያ ወር ላይ ለሚሆነው የፋሲካ በዓል ተዝቢው ዝግጅት እንዲደረግ ካህናት ታዘዋል:: የፋሲካ በዓል ደግሞ ከቂጣ በዓል ጋር የተያያዘ ነው (ዘፀ 12፥15፤ ዘሌ 23፥4-8 ይመ):: ቍጥር ሰባት እንዲሁም ብዜቱ የሆነው ዐሥራ አራት በዚህ አንቀጽ ውስጥ ተደጋግሞ ተጠቅሶአል::

ለሰባት ቀን በእሳት ለሚቀርብ መሥዋዕት የምግብ ቍርባን አዘጋጁ፤ ይህም ከመጠጥ ቍርባኑ ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ጋር ሆኖ በተጨማሪ ይቀርባል። [25]በሰባተኛው ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ የዘወትር ተግባርም አትሥሩበት።

### የሳምንቱ በዓል

28፥26-31 ተጓ ምብ - ዘሌ 23፥15-22፤ ዘዳ 16፥9-12

[26]“ ‘በየሳምንቱ በሚደረገው በዓል፣ አዲስ የእህል ቍርባን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) በምታቀርቡበት በፍሬ በኵራት ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ የዘወትር ተግባርም አትሥሩበት። [27]ሁለት ወይፈኖች፣ አንድ አውራ በግና ዓመት የሆናቸውን ሰባት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ሽታው *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ አድርጋችሁ የሚቃጠል መሥዋዕት አቅርቡ። [28]ከእያንዳንዱም ወይፈን ጋር ለእህል ቍርባን የሚሆን በዘይት የተለወሰ የኢፉ ሦስት ዐሥረኛ፣ ከአውራው በግ ጋር የኢፍ ሁለት ዐሥረኛ ልም ዱቄት ይቀርባል፤ [29]ከሰባቱም የበግ ጠቦቶች ከእያንዳንዳቸው ጋር የኢፉ አንድ ዐሥረኛ ልም ዱቄት ይቅረብ። [30]በተጨማሪም ማስተስረያ እንዲሆንላችሁ አንድ ተባዕት ፍየል አቅርቡ። [31]ከእህል ቍርባኑ ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት በተጨማሪ እነዚህን ከመጠጥ ቍርባናቸው ጋር አቅርቡ። እንስሳቱም እንከን የሌላቸው መሆናቸውን አረጋግጡ።

### የመለከት በዓል

29፥1-6 ተጓ ምብ - ዘሌ 23፥23-25

**29** “ ‘በሰባተኛው ወር በመጀመሪያው ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ የዘወትር ሥራም አትሥሩበት፤ ይህም የመለከት ድምፅ የምታሰሙበት ቀናችሁ ነው። [2]እንከን የሌለባቸውን አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግና ዓመት የሆናቸው ሰባት ተባዕት የበግ ጠቦቶች ሽታው *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ የሚቃጠል መሥዋዕት አድርጋችሁ አቅርቡ። [3]ከወይፈኑ ጋር ለእህል ቍርባን የሚሆን የኢፍ[ሀ] ሦስት ዐሥረኛ፣ ከአውራውም በግ ጋር የኢፍ ሁለት ዐሥረኛ[ለ]፣ በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት አቅርቡ፤ [4]ከእያንዳንዱም ሰባት የበግ ጠቦት ጋር በዘይት የተለወሰ የኢፍ አንድ ዐሥረኛ[ሐ] ልም ዱቄት አዘጋጁ። [5]ማስተስረያ እንዲሆናችሁም አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት በማድረግ በተጨማሪ አቅርቡ። [6]እነዚህ እንግዲህ በተደነገገው መሠረት ከእህል ቍርባናቸውና ከመጠጥ ቍርባናቸው ጋር በየዕለቱና በየወሩ ከሚቀርቡት የሚቃጠሉ መሥዋዕቶች ሌላ ተጨማሪ ሆነው፣ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ሽታቸው ደስ የሚያሰኝ በእሳት የሚቀርቡ መሥዋዕቶች ናቸው።

### የማስተስረያ ቀን

29፥7-11 ተጓ ምብ - ዘሌ 16፥2-34፤ 23፥26-32

[7]“ ‘በዚሁ በሰባተኛው ወር በዐሥረኛውም ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ ራሳችሁን አዋርዱ፤[መ] ሥራም አትሥሩ። [8]ሁሉም እንከን የሌለባቸው አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግና ዓመት የሆናቸው ሰባት ተባዕት የበግ ጠቦቶች፣ ሽታው *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ የሚቃጠል መሥዋዕት አድርጋችሁ አቅርቡ። [9]ከወይፈኑ ጋር ለእህል ቍርባን የሚሆን የኢፍ ሦስት ዐሥረኛ፣ ከአውራ በጉ ጋር የኢፍ ሁለት ዐሥረኛ በዘይት የተለወሰ ዱቄት አቅርቡ፤ [10]ከሰባቱ የበግ ጠቦቶችም ከእያንዳንዳቸው ጋር በዘይት የተለወሰ የኢፍ አንድ ዐሥረኛ ልም ዱቄት አዘጋጁ። [11]ማስተስረያ እንዲሆንም ለኀጢአት መሥዋዕት ከሚቀርበው እንዲሁም ከእህሉ ቍርባንና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ቀርቦ ከሚቃጠለው መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

### የዳስ በዓል

29፥12-39 ተጓ ምብ - ዘሌ 23፥33-43፤ ዘዳ 16፥13-17

[12]“ ‘በሰባተኛው ወር በዐሥራ አምስተኛው ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ የዘወትር ሥራ አትሥሩ፤ *ለእግዚአብሔርም* (ያህዌ) የሰባት ቀን በዓል አክብሩ። [13]ሁሉም እንከን የሌለባቸው ዐሥራ ሦስት ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ ሁለት ተባዕት የበግ ጠቦቶች የሚቃጠል መሥዋዕት በማድረግ ሽታው *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ደስ እንዲያሰኝ በእሳት አቅርቡ [14]ከዐሥራ ሦስቱ ወይፈኖች ከእያንዳንዳቸው ጋር የኢፍ ሦስት ዐሥረኛ፣ ከሁለቱ አውራ በጎችም ከእያንዳንዳቸው ጋር የኢፍ ሁለት ዐሥረኛ በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የእህል ቍርባን አቅርቡ፤ [15]እንዲሁም ከዐሥራ አራቱ ተባዕት የበግ ጠቦቶች ከእያንዳንዳቸው ጋር

28፥26 ቍ 18፤ ዘፀ 34፥22፤ 23፥16
28፥27 ቍ 19
28፥28 ቍ 12
28፥29 ቍ 13
28፥30 ቍ 15
28፥31 ቍ 3፥19
29፥1 ዘኍ 28፥18
29፥2 ቍ 36፤ ዘሌ 1፥3፡9፤ ዘኍ 28፥2፡3፡11
29፥3 ቍ 14፤ ዘኍ 28፥12
29፥4 ዘኍ 28፥13
29፥5 ዘኍ 28፥15
29፥6 ዘሌ 1፥9፤ ዘኍ 28፥2፡3፡5፡7፡11
29፥7 ዘፀ 31፥15፤ ሐሥ 27፥9
29፥8 ቍ 2
29፥9 ቍ 3፥18፤ ዘኍ 28፥12
29፥10 ዘኍ 28፥13
29፥11 ቍ 5፥6፤ ዘሌ 16፥3፤ ዘኍ 28፥15
29፥12 ዘሌ 23፥24፤ 1ነገ 8፥2፤ 12፥32
29፥13 ቍ 2፤ ዘኍ 28፥2፡3
29፥14 ቍ 3፤ ዘኍ 15፥6
29፥15 ቍ 4፤ ዘኍ 28፥13

[ሀ]3 ስድስት ተኩል ሊትር ያህል ነው።
[ለ]3 አራት ተኩል ሊትር ያህል ነው።
[ሐ]4 ሁለት ሊትር ያህል ነው።
[መ]7 ወይም ጹሙ

*28፥26-31፤* የቂጣ በዓል ከተደረገ ከአምሳ ቀን በኋላ፣ የመከር በዓል ይደረጋል (ዘሌ 23፥9-22 *ይመ*)፤ በአዲስ ኪዳን የተጠቀሰው (*ሐሥ* 2፥1)፣ “በዓለ ኀምሳ” የተባለው ቃል የተገኘው ከዚሁ “ከአምሳ” ቍጥር ነው።

*29፥1-6፤* በሰባተኛው ወር መጀመሪያ ላይ መለከት በመንፋት በዓል የተደረገ ከመሆኑም በላይ፣ በተቀደሰ በዓል እግዚአብሔርን ለማምለክ ወሩ ሁሉ ሥራ የበዛበት ወቅት ነበር (ዘሌ 23፥23-25 *ይመ*)። ከጊዜ በኋላም፣ በአይሁድ ልማድ ይህ በዓል የአዲስ ዓመት መታሰቢያ ነበር።

*29፥7-11፤* መለከት በመንፋት የሚደረገው በዓል ለኀጢአት ስርየት ቀን የሚያዘጋጅ ነው፤ ይህ ቀን ሕዝቡ ከሠራው ኀጢአት በመጽዳት በንስሓ የሚቀርብበትና በዓል የሚደረግበት ዕለት ነው (ዘሌ 16፤ 23፥26-32 *ይመ*)።

*29፥12-34* በሰባተኛው ወር መለከት በመንፋት በተደረገው በዓል በመጀመሪያው ቀን ነው፤ በዐሥረኛው ቀን የኀጢአት ስርየት ቀን የነበረ ሲሆን፣ በዐሥራ አምስተኛውም ቀን ለሰባት ቀናት የተከበረው የዳስ በዓል ተደርጓአል (ዘሌ 23፥33-44 *ይመ*)። በእያንዳንዱ ቀን የሚቀርበው መሥዋዕት ራሱን የቻለ ሥርዐት ነበረው።

የኢፍ አንድ ዐሥረኛ በዘይት የተለወሰ ልም ዱቄት የእህል ቍርባን አቅርቡ። [16]ከእህሉ ቍርባንና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[17]“ ‘በሁለተኛው ቀን ሁሉም እንከን የሌለባቸው ዐሥራ ሁለት ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ አራት ተባዕት የበግ ጠቦቶች አቅርቡ። [18]ከወይፈኖቹ፣ ከአውራ በጎቹና ከበግ ጠቦቶቹ ጋር በተወሰነው ቍጥር መሠረት የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን አብራችሁ አቅርቡ። [19]ደግሞም ከእህሉ ቍርባንና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ አውራ ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[20]“ ‘በሦስተኛው ቀን ሁሉም እንከን የሌለባቸው ዐሥራ አንድ ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ አራት ተባዕት የበግ ጠቦቶች አቅርቡ። [21]ከወይፈኖቹ፣ ከአውራ በጎቹና ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን በተወሰነው ቍጥር መሠረት አብራችሁ አቅርቡ። [22]ደግሞም ከእህሉ ቍርባኑና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[23]“ ‘በአራተኛው ቀን ሁሉም እንከን የሌለባቸው ዐሥር ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ አራት ተባዕት የበግ ጠቦቶች አቅርቡ። [24]ከወይፈኖቹ፣ ከአውራ በጎቹና ከጠቦቶቹ ጋር የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን በተደነገው ቍጥር መሠረት አቅርቡ። [25]ደግሞም ከእህሉ ቍርባኑና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[26]“ ‘በአምስተኛው ቀን ሁሉም እንከን የሌለባቸው ዘጠኝ ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ አራት ተባዕት የበግ ጠቦቶች አቅርቡ። [27]ከወይፈኖቹ፣ ከአውራ በጎቹና ከጠቦቶቹ ጋር የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን በተወሰነው ቍጥር መሠረት አቅርቡ። [28]ደግሞም ከእህሉ ቍርባኑና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[29]“ ‘በስድስተኛው ቀን ሁሉም እንከን የሌለባቸው ስምንት ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ አራት ተባዕት የበግ ጠቦቶች አቅርቡ። [30]ከወይፈኖቹ፣ ከአውራ በጎቹና ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን በተወሰነው ቍጥር መሠረት አቅርቡ። [31]ደግሞም ከእህሉ ቍርባንና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[32]“ ‘በሰባተኛው ቀን ሁሉም እንከን የሌለባቸው ሰባት ወይፈኖች፣ ሁለት አውራ በጎችና ዓመት የሆናቸው ዐሥራ አራት ተባዕት የበግ ጠቦቶች አቅርቡ። [33]ከወይፈኖቹ፣ ከአውራ በጎቹና ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን በተወሰነው ቍጥር መሠረት አቅርቡ። [34]ደግሞም ከእህሉ ቍርባንና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[35]“ ‘በስምንተኛው ቀን የተቀደሰ ጉባኤ አድርጉ፤ የዘወትር ሥራም አትሥሩ። [36]ሁሉም እንከን የሌለባቸው አንድ ወይፈን፣ አንድ አውራ በግና ዓመት የሆናቸው ሰባት ተባዕት የበግ ጠቦቶች የሚቃጠል መሥዋዕት በማድረግ ሽታው እግዚአብሔርን (ያህዌ) ደስ የሚያሰኝ ቍርባን በእሳት አቅርቡ። [37]ከወይፈኑ፣ ከአውራ በጉና ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የእህል ቍርባናቸውንና የመጠጥ ቍርባናቸውን በተወሰነው ቍጥር መሠረት አቅርቡ። [38]ደግሞም ከእህሉ ቍርባንና ከመጠጡ ቍርባን ጋር በመደበኛነት ከሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ሌላ አንድ ተባዕት ፍየል የኀጢአት መሥዋዕት አድርጋችሁ በተጨማሪ አቅርቡ።

[39]‘በስእለትና በበጎ ፈቃድ ከምታቀርቧቸው ቍርባኖች በተጨማሪ የሚቃጠሉ መሥዋዕቶቻችሁን፣ የእህል ቍርባኖቻችሁን፣ የመጠጥ ቍርባኖቻችሁንና የኅብረት መሥዋዕቶቻችሁን[1] በተወሰኑት በዓሎቻችሁ ላይ ለእግዚአብሔር (ለያህዌ) አቅርቡ።’ ”

[40]ሙሴም እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘውን ሁሉ ለእስራኤላውያን ነገራቸው።

## ስእለት

**30** ሙሴ ለእስራኤል የነገድ አለቆች እንዲህ አላቸው፤ “እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዘው ይህ ነው፤ [2]አንድ ሰው ለእግዚአብሔር (ለያህዌ) ስእለት በሚሳልበት ወይም አንድ ነገር ለማድረግ በመሐላ ራሱን ግዴታ ውስጥ በሚያስገባበት ጊዜ ቃሉን ሳያጥፍ ያለውን ሁሉ መፈጸም አለበት።

[1]39 በተለምዶ የደኅንነት መሥዋዕት ይባላል።

29፥16 ቍ5፡6፤ ዘኍ28፥15
29፥17 ቍ2፤ዘሌ 23፥36፤ዘኍ28፥3
29፥18 ቍ9፤ዘኍ 15፥4-12፤28፥7
29፥19 ቍ6፤ዘኍ 28፥3፡15
29፥20 ቍ17
29፥21 ቍ18
29፥35 ዘሌ23፥36
29፥36 ቍ2፤ ዘሌ1፥9
29፥39 ዘሌ1፥3፤ 3፥1፤7፥16፤23፥2፤ ዘኍ 6፥2፤1ዜና 23፥31፤2ዜና31፥3
30፥1 ዘኍ1፥4
30፥2 ዘዳ23፥21-23፤መሳ11፥35፤ኢዮ 22፥27፤መዝ22፥25፤ 50፥14፤61፥5፡8፤76፥ 11፤116፥14፤ምሳ20፥ 25፤መክ5፥4፡5፤ኢሳ 19፥21፤ዮና1፥16፤ 2፥9

29፥40 *ሙሴም ... ለእስራኤላውያን ነገራቸው፤* በበዓሉ መጨረሻ ላይ የተሰጠው የማጠቃለያ ሐሳብ ከሙሴ ወደ ኢያሱ ሥልጣን በማስተላለፍ ለሚደረገው ሂደት አስፈላጊ ነበር።

*30፥1-16፤* ይህ ዋና የብሉይ ኪዳን ክፍል ስእለትን በተመለከተ የተጠቀሰ ነው (ዘዳ 23፥21-23 ይመ)። ቸኩሉ ስእለት መሳል ተገቢ እንዳልሆነና (ከመክ 5፥1-7 ጋር ያነጻጽሩ) ለእግዚአብሔር የተሳሉትንም ነገር መፈጸም ተገቢ መሆኑን የገልጻል።

³"በአባቷ ቤት የምትኖር ሴት ልጅ ለእግዚአብሔር (ለያህዌ) ስእለት ብትሳል ወይም አንድ ነገር ለማድረግ በመሐላ ራሷን ግዴታ ውስጥ ብታስገባ፣ ⁴አባቷም መሳሏን ወይም ራሷን ግዴታ ውስጥ ማስገባቷን ሰምቶ ምንም ነገር ሳይላት ቢቀር ስእለቶቿ በሙሉ፣ ራሷንም ግዴታ ውስጥ ያስገባችባቸው ነገሮች ሁሉ መፈጸም ይኖርባቸዋል። ⁵አባቷ ይህንኑ ሰምቶ ከከለከላት ግን የትኛውም ስእለቷ ወይም ራሷን ግዴታ ውስጥ ያስገባችበት መሐላ አይያዝባትም፤ የከለከላት አባቷ ስለ ሆነ እግዚአብሔር (ያህዌ) ነጻ ያደርጋታል።

⁶"እንዲሁም ከተሳለች ወይም አምልጦአት ተናግራ ራሷን ግዴታ ውስጥ ካስገባች በኋላ ባል ብታገባ፣ ⁷ባሏም ሰምቶ ምንም ነገር ሳይላት ቢቀር ስእለቶቿ ወይም ራሷን ግዴታ ውስጥ ያስገባችባቸው ነገሮች መፈጸም ይኖርባቸዋል። ⁸ሆኖም ባሏ ይህንኑ ሰምቶ ከከለከላት ግን ለመፈጸም የተሳለችውንም ሆነ አምልጦአት ተናግራ ራሷን ግዴታ ውስጥ ያስገባችበትን ነገር ስለሚያስቀር እግዚአብሔር (ያህዌ) ከዚህ ነጻ ያደርጋታል።

⁹"ባሏ የሞተባት ወይም ከባሏ የተፋታች ሴት የትኛውም ስእለቷ ወይም የገባችበት ግዴታ ሁሉ የጸና ይሆናል።

¹⁰"ከባሏ ጋር የምትኖር ሴት ብትሳል ወይም አንድ ነገር ለማድረግ በመሐላ ራሷን ግዴታ ውስጥ ብታስገባና ¹¹ባሏም ይህንኑ ሰምቶ ምንም ነገር ባይላትና ባይከለክላት ግን ስእለቶቿም ሆኑ ለማድረግ ራሷን ግዴታ ውስጥ ያስገባችባቸው ነገሮች ሁሉ የጸኑ ይሆናሉ። ¹²ባሏ ሰምቶ እንዲቀሩ ካደረገ ግን ስእለቶቿንም ሆነ ለማድረግ ቃል የገባቻቸውን ነገሮች የመፈጸም ግዴታ የለባትም፤ ባሏ እንዲቀሩ ስላደረጋቸው እግዚአብሔር (ያህዌ) ነጻ ያደርጋታል። ¹³የትኛውንም ስእለቷን ወይም ራሷን ለመከላከል በመሐላ የታሰረችበትን ሁሉ ባሏ ሊያጸናው ወይም ሊያፈርሰው ይችላል። ¹⁴ይሁን እንጂ ባሏ ግን ስለ ጉዳዩ ከዕለት ወደ ዕለት ምንም ነገር ሳይላት ቢቀር ስእለቶቿን ወይም ራሷን ግዴታ ውስጥ ያስገባችባቸውን ነገሮች ሁሉ እያጸናላት ነው ማለት ነው፤ ስለ ነገሮቹ ሰምቶ ምንም ነገር ሳይላት በመቅረቱ አጽንቶላታል። ¹⁵ስለ ነገሮቹ ከሰማ በኋላ እንዲቀሩ ካደረገ ግን ለፈጸመችው በደል በኀላፊነት የሚጠየቀው ራሱ ነው።"

¹⁶እነዚህ እንግዲህ በባልና በሚስት፣ በአባትና አብራው በቤት ውስጥ በምትኖር ልጁ መካከል ያለውን ግንኙነት አስመልክቶ እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሙሴ የሰጠው ሥርዐቶች ናቸው።

## ምድያማውያንን መበቀል

**31** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን፤ ²"ለእስራኤላውያን ምድያማውያንን ተበቀልላቸው፤ ከዚያም ወደ ወገኖችህ ትከማቻለህ" አለው።

³ስለዚህ ሙሴ ሕዝቡን እንዲህ አላቸው፤ "ምድያማውያንን ለመውጋት እንዲሄዱና ስለ እግዚአብሔርም (ያህዌ) እንዲበቀሏቸው ከሰዎቻችሁ ጥቂቶቹን ለጦርነት አዘጋጁ። ⁴ከእያንዳንዱም የእስራኤል ነገድ አንዳንድ ሺህ ሰው ለጦርነቱ ላኩ።" ⁵ስለዚህ ከእስራኤል ጐሣዎች ተወጣጥቶ ከእያንዳንዱ ነገድ አንድ ሺህ በአጠቃላይ ዐሥራ ሁለት ሺህ ሰው ለጦርነት ተዘጋጀ። ⁶ሙሴም የቤተ መቅደሱን ንዋየ ቅዱሳትና ምልክት መስጫ የሆኑትን መለከቶች ከያዘው ከካህኑ ከአልዓዛር ልጅ ከፊንሐስ ጋር ከየነገዱ አንዳንድ ሺህ ሰው ለጦርነት ላከ።

⁷እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን ባዘዘው መሠረት ከምድያም ጋር ተዋጉ፤ ወንዱንም በሙሉ ፈጁት፤ ⁸ከተገደሉትም መካከል አምስቱ የምድያም ነገሥታት ኤዊ፣ ሮቄም፣ ሱር፣ ሑርና ሪባ ይገኙባቸዋል፤ የቢዖርን ልጅ በለዓምንም በሰይፍ ገደሉት። ⁹ከዚያም እስራኤላውያን

30፥4 ቍ7
30፥5 ቍ8፡12፡15
30፥6 ዘሌ5፥4
30፥8 ቍ5፤ዘዳ3፥6
30፥12 ኤፌ5፥22፤ ቈላ3፥18
30፥15 ቍ5
31፥2 ዘፍ25፥2፤ ዘኍ20፥26
31፥3 መሳ11፥36፤ 1ሳሙ24፥12፤2ሳሙ4፥8፤22፥48፤መዝ94፥1፤149፥7፤ኢሳ34፥8፤ኤር11፥20፤46፥10፤ሕዝ25፥17
31፥5 ቍ6፡21
31፥6 ቍ5፤ዘፀ6፥25፤ዘኍ10፥2፤14፥44
31፥7 ዘኍ25፥16፤ ዘዳ20፥13፤መሳ21፥11፤1ነገ11፥15፡16
31፥8 ዘፍ34፥29፤ ዘኍ22፥5፤24፥14፤25፥15፤ኢሱ13፥21፤22

*30፥3-5፤* በአባቷ ቤት ያለች ያላገባች ልጃገረድ የምትሳለውን ስእለት አባቷ ሊፈጽምላት ይገባል። በዚህ ስፍራ የተጠቀሰውና ከእርሱ ቀጥሎ ያለው ሕግ የወጣው፣ ሴት እንዳትጐዳ መከላከያ ለማበጀት ይሆናል፤ ይህም በጥንት የቅርብ ምሥራቅ አገር ልማድ ሴት አንዳንድ ጊዜ ያለ ረዳት እስከምትቀር ድረስ ከባድ በሆነ የኀብረተ ሰብ ተጽእኖ ሥር ስለምትሆን ነበር።

*30፥6-8፤* ያገባች ሴት የምትሳለው ስእለት በባሏ መፈጸም አለበት።

30፥9 *ባሏ የሞተባት ወይም ከባሏ የተፋታች ሴት፣* በዚህ ሁኔታ ያለች ሴት ስእለት መሳሉ በቀጥታ እርሷን የሚመለከት ስለ ሆነ ራሷ የግድ መፈጸም ይገባታል።

*30፥10-15፤* በባልና በሚስት ግንኙነት ደረጃ ስእለት መሳል ሊያስከትል የሚችል ውስብስብ ሁኔታን የሚያሳይ ተጨማሪ ምሳሌ ነው። እንደዚህ ዐይነት ውስብስብ ነገር ጐልቶ የታየው በሰለጰዓድ ሴት ልጆች ዘንድ በተፈጠረው ሁኔታ ሊሆን ይችላል (27፥1-11)። በመጨረሻ በሕግ መልክ ለሰፈረው ለዚህ ነገር ምክንያት ሆኖ አንዱ ጉዳይ ከሌላው ጋር ተያይዞ እንደ መጣ ተገልጾአል። እስከ አዲስ ኪዳን ባሉት ዓመታት፣ ስእለትን በተመለከተ ይሰጥ የነበረው ሕጋዊ ውሳኔ ይበልጥ ውስብስብ ሆኖ ነበር። ከመሐላ ጋር በተያያዘ አንድ ሰው ውስብስብ ሁኔታ ውስጥ ራሱን እንዳያስገባ (ማቴ 5፥33-37) ኢየሱስ የተናገረው ነገር ለዚህ ችግር መፍትሔ ነው።

*31፥1-24፤* ሙሴ ከመሞቱ በፊት ሊያደርጋቸው ከሚገባው የመጨረሻ ነገሮች እንደ አንዱ ሆኖ እንዲፈጽመው የተፈለገው፣ እግዚአብሔር በምድያማውያን ላይ ቅዱስ ጦርነት ማወጁን እንዲያሳውቅ ነበር። የዝሙት ኀጢአት እንዲሠሩና በበአል ፌጎር እንዲያመልኩ እስራኤላውያንን በማታለላቸው፣ እግዚአብሔር በምድያማውያን ላይ ያወጀው፣ "የእግዚአብሔር በቀል" ጦርነት እንጂ ሙሴ በቅናት ተነሣስቶ ያደረገው አልነበረም (25፥16-18 ይመ፤ በም 31 ላይ የተገለጸው ቍጣ መባባስ ምክንያት የሆነችው ምድያማዊቷ ሴት ከስቢ በዚህ ስፍራ ተጠቅሳለች)።

31፥2 *ወደ ወገኖችህ ትከማቻለህ፤* ለዘብ ባለ አነጋገር ሙሴ መሞቱን ለመግለጽ ነው (ዘፍ 25፥8፡17፤ 35፥29 ይመ)።

31፥4 *ከእያንዳንዱም የእስራኤል ነገድ አንዳንድ ሺህ ሰው፣* ይህን ቅዱስ ጦርነት በተመለከተ እያንዳንዱ ነገድ እኩል የሆነ ሸክምና ኀላፊነት እንዲሰማው ማድረግ አስፈላጊ ነበር።

31፥6 *ፊንሐስ፤* ለእግዚአብሔር ክብር ከመቅናቱ የተነሣ ዘንበሪንና ከስቢን ገደላቸው (25፥8)። ይህ ቅዱስ ጦርነት መሆኑን ለማሳየት በጦርነቱ ላይ የሚያገለግሉ ንዋየ ቅዱሳትን የመጠበቅ ኀላፊነት ለእርሱ ተሰጠ፤ የ10፥3 ማብ ይመ።

31፥7 *እግዚአብሔር ሙሴን ባዘዘው መሠረት፤* ይህ የእግዚአብሔር ጦርነት ነበር።

31፥8 *በለዓምንም... ገደሉት፤* ከእግዚአብሔር ሕግ ውጪ በአልን እንዲያመልኩ እስራኤላውያንን ለማታለል ዋና አነሣሽ የነበረው ሰው ስም በም 25 ላይ አልተጠቀሰም። ነገር ግን በዚያ ከሞቱ ሰዎች አንዱ እንደ ሆነ ተጠቅሶአል። በለዓም የጕንቁላ ሥራ

የምድያማውያን ሴቶችና ሕፃናት ማረኩ፤ የቀንድ ከብቶቻቸውን፣ የበግና የፍየል መንጋዎቻቸውን ሁሉ ነዱ፤ ሀብታቸውንም በሙሉ ወሰዱ። [10]ምድያማውያኑ የሚኖሩባቸውን ከተሞች ሁሉ ሰፈሮቻቸውንም በሙሉ አቃጠሉ። [11]ሰውና እንስሳትን ጨምሮ የማረኩትንና የዘረፉትን ሁሉ እንዳለ አጋዙት። [12]የማረኳቸውን ሰዎች፣ የነዱአቸውን እንስሳትና የዘረፉትን ሀብት በሙሉ፣ ከኢያሪኮ[m] ማዶ፣ በዮርዳኖስ አጠገብ፣ በሞዓብ ወዳለው፣ ሙሴና ካህኑ አልዓዛር እንዲሁም መላው የእስራኤላውያን ማኅበር ወዳሉበት ሰፈራቸው አመጡአቸው።

[13]ሙሴ፣ ካህኑ አልዓዛርና የማኅበረ ሰቡ መሪዎች በሙሉ ሊቀበሉአቸው ከሰፈር ወጡ። [14]ሙሴም ከጦርነት በተመለሱት በሰራዊቱ አዛዦች ማለትም በሻለቆችና በመቶ አለቆች ላይ ተቈጣ።

[15]እርሱም እንዲህ አላቸው፤ "ሴቶችን ሁሉ እንዴት በሕይወት ትተውአቸዋላችሁ?" [16]የበለዓምን ምክር ተቀብለው በፌጎር በተፈጸመው ድርጊት እስራኤላውያን *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዲመለሱና *የእግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሕዝብ እንዲቀሠፍ ያደረጉት እነርሱ ናቸው። [17]አሁንም ወንዶቹን ልጆች ሁሉ፣ ወንድ ያወቁትንም ሴቶች በሙሉ ግደሉዋቸው፤ [18]ነገር ግን ወንድ ያላወቁትን ልጃገረዶች ሁሉ ለራሳችሁ አስቀሩአቸው።

[19]"ከእናንት መካከል ሰው የገደለ ወይም የተገደለውን የነካ ሁሉ ከሰፈር ውጭ ሰባት ቀን ይቈይ። በሦስተኛውና በሰባተኛው ቀን ራሳችሁንና ምርኮኞቻችሁን አንጹ። [20]ማናቸውንም ልብስ እንዲሁም ከቈዳ፣ ከፍየል ጠጕር ወይም ከዕንጨት የተሠራ ማንኛውንም ነገር አንጹ።"

[21]ከዚያም ካህኑ አልዓዛር ወደ ጦርነት ሄደው የነበሩትን ወታደሮች እንዲህ አላቸው፤ "*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለሙሴ የሰጠው የሕጉ ሥርዐት ይህ ነው፤ [22]ወርቅ፣ ብር፣ ናስ፣ ብረት፣ ቈርቈሮ፣ እርሳስ [23]እንዲሁም እሳትን መቋቋም የሚችል ማንኛውም ነገር በእሳት ውስጥ ማለፍ አለበት፤ ከዚያም ንጹሕ ይሆናል፤ ይህም ሆኖ መንጻት አለበት። እሳትን መቋቋም የማይችል ማንኛውም ነገር በዚሁ ውሃ ውስጥ ማለፍ አለበት። [24]በሰባተኛው ቀን ልብሳችሁን እጠቡ፤ ትነጻላችሁም፤ ከዚያም ወደ ሰፈር መግባት ትችላላችሁ።"

## ምርኮን መከፋፈል

[25]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [26]"አንተ፣ ካህኑ አልዓዛርና በማኅበረ ሰቡ ውስጥ ያሉት የየቤተ ሰቡ አለቆች ሆናችሁ የተማረከውን ሕዝብና እንስሳት ሁሉ ቍጠሩ። [27]ምርኮውንም ለሁለት ክፍላችሁ በጦርነቱ ለተካፈሉት ወታደሮችና ለቀረው ማኅበረ ሰብ አከፋፍሉት። [28]በጦርነቱ ከተካፈሉት ወታደሮች ድርሻ ላይ፣ ከሰውም ሆነ ከቀንድ ከብት፣ ከአህያ፣ ከበግ ወይም ከፍየል ከየአምስት መቶው አንዱን *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ግብር አውጣ። [29]ይህንንም ግብር ከድርሻቸው ላይ ወስደህ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፈንታ በማድረግ ለካህኑ ለአልዓዛር ስጠው። [30]ከእስራኤላውያን እኩሌታ ድርሻ ደግሞ ከሰውም ይሁን ከቀንድ ከብት፣ ከአህያ፣ ከበግ፣ ከፍየል ወይም ከሌሎች እንስሳት ከየአምሳው አንዳንድ መርጠህ፣ *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ማደሪያ ድንኳን በኀላፊነት ለሚጠብቁ ሌዋውያን ስጣቸው።" [31]ሙሴና ካህኑ አልዓዛርም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው አደረጉ።

[32]ወታደሮቹ ማርከው ከወሰዱለት ምርኮ ውስጥ የቀረው ይህ ነበር፤ ስድስት መቶ ሰባ አምስት ሺህ በግ፣ [33]ሰባ ሁለት ሺህ የቀንድ ከብት፣ [34]ሥልሳ አንድ ሺህ አህያ [35]ወንድ ያላወቁ ሠላሳ ሁለት ሺህ ሴቶች።

[36]በጦርነቱ ላይ የነበሩት ወታደሮች እኩሌታ ድርሻ ይህ ነበር፤

ሦስት መቶ ሠላሳ ሰባት ሺህ አምስት መቶ በግ፤ [37]ከነዚህም *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የተሰጠ ግብር ስድስት መቶ ሰባ አምስት ነበር።

[38]ሠላሳ ስድስት ሺህ የቀንድ ከብት፣ ከነዚህም *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የተሰጠው ግብር ሰባ ሁለት ነበር።

[39]ሠላሳ ሺህ አምስት መቶ አህያ፣ ከነዚህም *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የተሰጠው ግብር ሥልሳ አንድ ነበር።

[40]ዐሥራ ስድስት ሺህ ሰው፤ ከነዚህም *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የተሰጠው ግብር ሠላሳ ሁለት ነበር።

[41]ሙሴም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዳዘዘው *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ድርሻ የሆነውን ግብር ለአልዓዛር ሰጠው።

[42]ሙሴ ከዘመቱት ሰዎች የለየው የእስራኤላውያን እኩሌታ ድርሻ ማለትም፣ [43]የማኅበረ ሰቡ ድርሻ ይህ ነበር፤ ሦስት መቶ ሠላሳ ሰባት ሺህ አምስት መቶ በግ፣ [44]ሠላሳ ስድስት ሺህ የቀንድ ከብት፣ [45]ሠላሳ ሺህ አምስት መቶ አህያ፣ [46]ዐሥራ ስድስት ሺህ ሰው። [47]ከእስራኤላውያን እኩሌታ ድርሻ ላይ፣

[m]12 በዕብራይስጥ *የኢያሪኮ ዮርዳኖስ* ማለት ሲሆን፣ ይህም የዮርዳኖስ ወንዝ የጥንት ስም ሳይሆን አይቀርም።

31፥9 ቍ15፤ዘፍ 34፥29
31፥10 ዘፍ25፥16፤ ኢሱ6፥24፤8፥28፤11፥11፤መሳ18፥27፤1ዜና 6፥54፤መዝ69፥25፤ ሕዝ25፥4
31፥11 ቍ26፤ ዘዳ20፥14፤2ዜና28፥8
31፥12 ቍ32፡53፤ ዘፍ49፥27፤ዘፀ15፥9፤ ዘኍ22፥1፤27፥2
31፥14 ቍ48፤ዘፀ 18፥21፤ዘዳ1፥15፤ 2ሳሙ18፥1
31፥16 ዘኍ22፥5፤ 23፥28፤24፥14፤25፥1-9፤14፥37፤2ጴጥ2፥15
31፥17 ዘዳ7፥2፤20፥16-18፤መሳ21፥11
31፥19 ዘሌ21፥1፤ ዘኍ19፥12፡16
31፥20 ዘሌ11፥32፤ ዘኍ19፥19
31፥21 ቍ5
31፥22 ኢሱ6፥19፤ 22፥8
31፥23 ዘኍ8፥7፤ 1ቆሮ3፥13
31፥24 ዘሌ11፥25፤ 14፥8
31፥26 ቍ11፡12፤ ዘኍ1፥4፡19
31፥27 ኢሱ22፥8፤ 1ሳሙ25፥13፤ 30፥24
31፥28 ቍ37-41፤ ዘኍ18፥21
31፥30 ዘኍ3፥7፤ 18፥3
31፥32 ቍ12
31፥37 ቍ38-41
31፥41 ቍ21፡28፤ ዘኍ5፥9፤18፥8

ወይም አስማት በመጠቀም (ም 22-24) ሊያደርግ ያልቻለውን ነገር፣ ምድያማውያንን ክፉ ምክር በመምከር ግብ መትቶለታል (ቍ 16)።

*31፥9-18፤* ወታደሮቹ ምድያማውያን ወንዶችን ሲገድሉ ሴቶችንና ልጆችን ማርከው ወሰዱ። በፌጎር ነውር ያልተሳተፉ ደናግል የሆኑ ሴቶች ብቻ እንዲሳተፉ ሙሴ አዘዘ፤ በእስራኤል የምርኮ መብትም ላይ ችግር ስለሚፈጥር፣ ነውረኛ የሆኑትን ሴቶችና ወንዶች ልጆች እንዲሞቱ ተደረገ (ቍ 15-17)።

*31፥19-24፤* ይህ ቅዱስ ጦርነት እንደ መሆኑ ሰዎች (ቍ 19-20) እና ዕቃዎቹ (ቍ 21-24) ሁለቱም ይነጹ ዘንድ አስፈላጊ ነበር (ከ19፥11-13 ጋር ያነጻጽሩ)።

*31፥26-35፤* በጦርነቱ ከተማረኩ ነገሮች የጦርነቱ ባለቤት ለሆነው ለእግዚአብሔር የሚገባውን ድርሻ በመስጠት (ቍ 28) ወደ ሰልፍ ለወጡና በማኅበሩ መካከል ሳይወጡ ለቀሩ ሰዎችም እኩል ማካፈል፣ የዚህ ቅዱስ ጦርነት ሌላው ገጽታው ነበር።

ሙሴ እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዳዘዘው ከየአምሳው ሰውና እንስሳ አንዳንድ መርጦ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ማደሪያ ድንኳን በኀላፊነት ለሚጠብቁ ሌዋውያን ሰጣቸው።

48ከዚያም በኋላ በሰራዊቱ ክፍሎች ላይ የተሾሙት የሻለቆችና የመቶ አለቆች ወደ ሙሴ ቀርበው፣ 49እንዲህ አሉት፤ “እኛ አገልጋዮችህ በእጃችን ሥር ያሉትን ወታደሮች ቈጥረናል፤ አንድም የጐደለ የለም። 50ስለዚህ እያንዳንዳችን ያገኘነውን የወርቅ ጌጣ ጌጥ፣ የእግር ዐልቦዎች፣ የእጅ አንባሮች፣ የጣት ቀለበቶች፣ የጆሮ ጒትቻዎችና የዐንገት ሐብሎች በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ማስተስረያ እንዲሆንን መባ አድርገን ለእግዚአብሔር (ያህዌ) አምጥተናል።”

51ሙሴና ካህኑ አልዓዛር በጌጣ ጌጥ መልክ የተሠራውን ወርቅ ሁሉ ተቀበሉአቸው። 52ሙሴና አልዓዛር ከሻለቆቹና ከመቶ አለቆቹ በመቀበል ስጦታ አድርገው ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ያቀረቡት ወርቅ ዐሥራ ስድስት ሺህ ሰባት መቶ ሃምሳ ሰቅል[ዐ] መዘን። 53እያንዳንዱም ወታደር ለራሱ የወሰደው ምርኮ ነበረው። 54ሙሴና ካህኑ አልዓዛር ወርቁን ከሻለቆቹና ከመቶ አለቆቹ ተቀብለው በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ለእስራኤላውያን መታሰቢያ እንዲሆን ወደ መገናኛው ድንኳን አመጡት።

## ከዮርዳኖስ ማዶ ያሉ ነገዶች

**32** እጅግ ብዙ የሆነ የቀንድ ከብት፣ የበግና የፍየል መንጋዎች የነበሩአቸው የሮቤልና የጋድ ነገዶች የኢያዜርና የገለዓድ ምድር ለከብት ምቹ ስፍራዎች መሆናቸውን አዩ። 2ስለዚህ ወደ ሙሴ፣ ወደ ካህኑ ወደ አልዓዛርና ወደ ማኅበረ ሰቡ መሪዎች መጥተው እንዲህ አሉ፤ 3“አጣሮት፣ ዲቦን፣ ኢያዜር፣ ኒምራ፣ ሐሴቦን፣ ኤልያሊ፣ ሰባማ፣ ናባውና፣ ባያን፣ 4እግዚአብሔር (ያህዌ) በእስራኤል ሕዝብ ፊት እንዲሸንፍ ያደረገው ይህ ሁሉ ምድር ለከብት ምቹ ነው፤ እኛ አገልጋዮችህም ከብቶች አሉን።” 5“በፊትህ ሞገስ ያገኘን ከሆነ ይህ ምድር ለእኛ ለአገልጋዮችህ በርስትነት ይሰጠን፤ ዮርዳኖስንም እንድንሻገር አታድርገን” አሉ።

6ሙሴም የጋድንና የሮቤልን ነገዶች እንዲህ አላቸው፤ “እናንተ እዚህ ተቀምጣችሁ ወገኖቻችሁ ወደ ጦርነት ይሂዱ? 7እስራኤላውያን ተሻግረው እግዚአብሔር (ያህዌ) ወደ ሰጣቸው ምድር እንዳይገቡ ተስፋ የምታስቈርጧቸው ለምድን ነው? 8አባቶቻችሁ ምድሪቱን እንዲሰልሉ ከቃዴስ በርኔ በላክኋቸው ጊዜም ያደረጉት ይህንኑ ነበር። 9ወደ ኤሽኮል ሸለቆ ሄደው ምድሪቱን ካዩ በኋላ፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) ወደ ሰጣቸው ምድር እንዳይገቡ እስራኤላውያንን ተስፋ አስቈረጧቸው። 10በዚያም ቀን የእግዚአብሔር (ያህዌ) ቍጣ ነደደ፤ እንዲህም ሲል ማለ፤ 11‘በፍጹም ልባቸው ስላልተከተሉኝ ከግብፅ ከወጡት፣ ዕድሜያቸው ሃያ ዓመትና ከዚያ በላይ የሆናቸው ሰዎች አንዳቸውም ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ ልሰጥ በመሐላ ቃል የገባሁላቸውን ምድር አያዩዋትም፤ 12እግዚአብሔርን (ያህዌ) በፍጹም ልባቸው ተከትለውታልና፣ ከቄኔዛዊው ከዮፎኒ ልጅ ከካሌብና ከነዌ ልጅ ከኢያሱ በስተቀር አንዳቸውም አያዩዋትም።’ 13የእግዚአብሔርም (ያህዌ) ቍጣ በእስራኤል ላይ ስለ ነደደ፣ በፊቱ ክፉ ነገር ያደረገው ያ ትውልድ በሙሉ እስኪያልቅ ድረስ አርባ ዓመት በምድረ በዳ እንዲንከራተቱ አደረጋቸው።

14“እናንት የኀጢአተኞች ልጆች ይኸው በአባቶቻችሁ እግር ተተክታችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ) በእስራኤል ላይ ይበልጥ እንዲቈጣ ታደርጋላችሁ። 15እርሱን ከመከተል ብትመለሱ አሁንም ይህን ሁሉ ሕዝብ በምድረ በዳ ይተወዋል፤ ለሚደርስበትም ጥፋት ምክንያቱ እናንተው ትሆናላችሁ።”

16ከዚህ በኋላ ወደ እርሱ ቀርበው እንዲህ አሉት፤ “እዚህ ለከብቶቻችን በረቶች፣ ለሴቶቻችንና ለልጆቻችን ከተሞች መሥራት እንወዳለን፤ 17ይሁን እንጂ ወደ ስፍራቸው እስክናገባቸው ድረስ ታጥቀንና በእስራኤላውያን ፊት ግንባር ቀደም ሆነን ለመሄድ ዝግጁ ነን፤ በዚህም ጊዜ ሴቶቻችንና ልጆቻችን በምድሪቱ ላይ ካሉት ነዋሪዎች እንዲጠበቁ በተመሸጉ ከተሞች ይኖራሉ። 18እኛም እያንዳንዱ እስራኤላዊ ርስቱን እስኪወርስ ድረስ ወደየቤታችን አንመለስም። 19ድርሻችንን ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተ ምሥራቅ ስለ ገኘን፣ ከዮርዳኖስ ማዶ ከእነርሱ ጋር የምንካፈለው አንዳችም ርስት አይኖርም።”

20ከዚያም ሙሴ እንዲህ አላቸው፤ “ይህን ብታደርጉ ማለትም በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ታጥቃችሁ ለጦርነት ብትዘጋጁ፣ 21እንዲሁም ጠላቶቹን ከፊቱ አሳዶ እስኪያስወጣ ድረስ ሁላችሁም በእግዚአብሔር ፊት ለጦርነት ዝግጁ ሆናችሁ ዮርዳኖስን ብትሻገሩ፣ 22ምድሪቱ ለእግዚአብሔር (ያህዌ) ከተገዛች በኋላ

ዐ52 አንድ መቶ ዘጠና ኪ.ግ. ያህል ነው።

31፥48 ቍ14
31፥49 ዘኍ1፥19፤ ኤር23፥4
31፥50 ዘፀ30፥16
31፥53 ዘፍ34፥29፤ ዘዳ20፥14
31፥54 ዘፀ27፥21፤ 28፥12፤40፥2
32፥1 ቍ24፥36፤ ዘፍ31፥21፤ዘፀ12፥38፤ ዘኍ21፥32፤መሳ5፥16
32፥2 ዘሌ4፥22፤ ዘኍ27፥2
32፥3 ቍ1፥34፤36፤ 37፤38፤ዘኍ21፥25፤ 30፤33፤47፤ዘዳ32፥49 ፥34፥1፤ኢሱ13፥17፤ 19፤27፤16፥2፤7፥18፥3 ፤ዘሌ5፥8፤ኢሳ15፥4፤ 16፥8፤9፤ኤር48፥32፤ 34፤ሕዝ25፥9
32፥4 ዘኍ21፥34፤ ዘፀ12፥38
32፥5 ዘኍ13፥29
32፥7 ዘኍ13፥27-14፥4
32፥8 ዘኍ13፥3፤ 26፤ዘዳ1፥19-25
32፥9 ዘኍ13፥23፤ ዘዳ1፥24
32፥10 ዘኍ11፥1፤ 14፥20-23
32፥11 ዘፀ30፥14፤ ዘኍ1፥1፤14፥23፤ 28-30
32፥12 ዘኍ14፥24፤ 30፤መዝ63፥8
32፥13 ዘፀ4፥14፤ ዘኍ14፥28-35፤ 26፥64፡65
32፥14 ቍ10፤ዘዳ 1፥34፤መዝ78፥59
32፥15 ዘዳ30፥17-18፤2ዜና7፥20
32፥16 ቍ24፥36፤ ዘፀ12፥38፤ዘዳ3፥19፤ 1ሳሙ24፥3፤መዝ 50፥9፤78፥70
32፥17 ዘኍ22፥4፤ ዘዳ3፥18፤20፤ኢሱ 4፥12፡13
32፥18 ኢሱ22፥1-4
32፥19 ቍ22፥29፤ ዘኍ21፥33፤ኢሱ 12፥1፤22፥7
32፥20 ቍ17
32፥21 ቍ17
32፥22 ዘሌ14፥34፤ ዘዳ3፥18-20፤ኢሱ22፥4

32፥1 *የሮቤልና የጋድ ነገዶች*፤ ከዮርዳኖስ ማዶ የሚገኘውን ሰፊና ለም የግጦሽ መሬት ለማግኘት ስለጓጉ የእነዚህ ሁለት ነገድ መሪዎች በዚያ ለመስፈርና ዮርዳኖስን እንዳይሻገሩ ጥያቄ አቀረቡ፡ ይህም አካባቢ በጦርነት የተገኘ የእግዚአብሔር ስጦታ ነበር።

32፥8 *አባቶቻችሁ... ያደረጉት ይህንኑ ነገር*፤ ከነዓንን ድል ለማድረግ እነዚህ ሁለት ነገዶች ከማኅበሩ ሁሉ ጋር ይቈዩ ዘንድ ወደ ኋላ ማለታቸው፣ ወደ ምድሪቱ ላለመግባት የአጠቃላይ ዐመፅ መነሻ እንዳይሆን የሙሴ ሥጋት ነበር። ይህ ከሆነ፣ የቃዴስ ውድቀት (ም 13-14) እንደ ገና ይደገማል ማለት ነው። ከሁሉም በላይ ከነዓናውያንን ድል ማድረግ የእስራኤላውያን ሁሉ ተልእኮ ነበር።

32፥17 *ታጥቀን... ለመሄድ ዝግጁ ነን*፤ መሬቱን ድል ለማድረግ ያግዙ ዘንድ ያለባቸውን ኀላፊነት ከመወጣት ወደ ኋላ የማለት ሐሳብ እንደሌላቸው የሮቤልና የጋድ ነገድ መሪዎች ለሙሴ ሊያረጋግጡ ፈለጉ፤ ከወንድሞቻቸው ጋር ለጦርነት በመውጣቱ ላይ የተስማሙ ሲሆን፣ ቤተ ሰቦቻቸውንና ከብቶቻቸውን ግን ምርኳቸው በሆነው ቦታ ለመተው ወሰኑ።

ልትመለሱ ትችላላችሁ፤ *ለእግዚአብሔርና* (ያህዌ) ለእስራኤል ካለባችሁም ግዴታ ነጻ ትሆናላችሁ፤ ይህችም ምድር *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ርስታችሁ ትሆናለች::

[23]"ይህን ባታደርጉ ግን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ትበድላላችሁ፤ ኀጢአታችሁ እንደሚያገኛችሁም ዕወቁ:: [24]ለሴቶቻችሁና ለልጆቻችሁ ከተሞች፣ ለበግና ለፍየል መንጎቻችሁም ጒረኖች ሥሩላቸው፤ የገባችሁበትን የተስፋ ቃል ግን ፈጽሙ::"

[25]የጋድና የሮቤል ሰዎች ሙሴን እንዲህ አሉት፤ "እኛ አገልጋዮችህ ጌታችን ያዘዘንን እንፈጽማለን:: [26]ልጆቻችንና ሚስቶቻችን፣ የበግና የፍየል እንዲሁም የከብት መንጎቻችን እዚሁ በገለዓድ ከተሞች ይቀራሉ፤ [27]ባሮችህ ግን ልክ ጌታችን እንዳለው እያንዳንዱ ሰው ለጦርነት ዝግጁ ሆኖ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ለመዋጋት እንሻገራለን::"

[28]ከዚያም ሙሴ ለካህኑ ለአልዓዛር፣ ለነዌ ልጅ ለኢያሱና ለእስራኤል ነገድ ቤተ ሰብ አለቆች እነርሱን አስመልክቶ ትእዛዝ ሰጠ፤ [29]እንዲህም አላቸው፤ "የጋድና የሮቤል ወንድ ሁሉ፣ እያንዳንዱ ለጦርነት በመዘጋጀት *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ከእናንተ ጋር ዮርዳኖስን የሚሻገር ከሆነ፣ ምድሪቱም በእጃችሁ ስትገባ የገለዓድን ምድር ርስት አድርጋችሁ ስጧቸው:: [30]ለጦርነት ተዘጋጅተው ከእናንተ ጋር ካልተሻገሩ ግን፣ ርስታቸውን አብረዋችሁ በከነዓን መካፈል አለባቸው::"

[31]የጋድና የሮቤል ሰዎች እንዲህ ሲሉ መለሱለት፤ "ባሪያዎችህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ያለውን ያደርጋሉ፤ [32]ለጦርነት ዝግጁ ሆነን *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ወደ ከነዓን እንሻገራለን፤ የምንወርሰው ርስት ግን ከዮርዳኖስ ወዲህ እዚሁ ይሆናል::"

[33]ከዚያም ሙሴ፣ የአሞራውያንን ንጉሥ የሴዎንን ግዛትና የባሳንን ንጉሥ የዐግን ግዛት ማለትም ምድሪቱንና ከነከተሞቿ በዙሪያዋ ያለውን ግዛት በሙሉ ለጋድና ለሮቤል ነገዶች እንዲሁም ለዮሴፍ ልጅ ለምናሴ ነገድ እኩሌታ ሰጣቸው::

[34]የጋድ ልጆች፣ ዲቦንን፣ አጣሮትን፣ አሮዔርን፣ [35]ዓጥሮትሾፋንን፣ ኢያዜርን፣ ዮግብሃን፣ [36]ቤትነምራንና ቤትሃራንን የተመሸጉ ከተሞች አድርገው ሠሩአቸው፤ እንዲሁም ለበግና ለፍየል መንጎቻቸው ጒረኖዎች አበጁላቸው:: [37]የሮቤልም ልጆች ሐሴቦንን፣

32፥23 ዘፍ4፥7፤ኢሳ 3፥9
32፥24 ቍ1:16፤ ዘኍ30፥2
32፥25 ቍ29፤ኢሱ 1፥16:18፤22፥2
32፥26 ቍ16:24፤ ኢሱ1፥14፤12፥2፤ 22፥9፤2ሳሙ2፥9፤ 1ዜና5፥9
32፥27 ቍ17:21
32፥28 ቍ29፤ዘኍ 1፥16፤11፥28ዘዳ 3፥18-20፤ኢሱ1፥13
32፥29 ቍ19፤ዘኍ 22፥4
32፥30 ቍ23:29:32
32፥31 ቍ29
32፥32 ቍ17:30፤ ኢሱ12፥6
32፥33 ቍ19፤ዘኍ 21፥21:24፤34፥14፤ ዘዳ2፥26፤36፤ኢሱ 1፥12፤12፥5:6፤13፥ 24-28፤1ሳሙ13፥7
32፥34 ዘዳ2፥36፤ 3፥12፤4፥48፤ኢሱ12፥ 2፤13፥9፤መሳ11፥26፤ 1ሳሙ30፥28፤1ዜና 5፥8፤ኤር48፥19
32፥35 ቍ3፤ መሳ8፥11
32፥36 ቍ1:3
32፥37 ቍ3፤ዘኍ 21፥25፤ኢሱ13፥19፤ 1ዜና6፥76፤ኤር48፥1: 23፤ሕዝ25፥9
32፥38 ቍ3፤ኢሳ 15፥2፤ኤር48፥1:22
32፥39 ዘፍ10፥16፤ 50፥23፤ዘኍ26፥29፤ ዘዳ2፥36
32፥40 ዘፍ50፥23፤ ዘዳ3፥15
32፥41 ዘዳ3፥14፤ ኢሱ13፥30፤መሳ10፥ 4፤1ዜና2፥23፤1ነገ 4፥13
32፥42 መሳ8፥11፤ 1ዜና2፥23፤1ሳሙ15፥ 12፤2ሳሙ18፥18፤ መዝ49፥11፤ኢሳ 22፥16፤56፥5
33፥1 ዘፀ4፥16፤ 6፥26፤17፥1፤40፥36፤ ዘኍ1፥1
33፥2 ቍ1፤ዘፀ 17፥14
33፥3 ዘፍ47፥11፤ዘፀ 14፥8፤ዘኍ10፥2፤ ኢሱ5፥10
33፥4 ዘፀ4፥23፤12፥ 12፤2ዜና24፥24፤ኤር 15፥3፤ሕዝ14፥21
33፥5 ዘፀ12፥37

ኤልያሊንና ቂርያታይምን [38]እንዲሁም ስማቸው የተለወጠውን ናባውን፣ በአልሜዎንን፣ ሴባማንን ዐደሱ፤ ሳደሷቸውም ከተሞች ስም አወጡላቸው::

[39]የምናሴ ልጅ የሆነው የማኪር ዘሮች ወደ ገለዓድ ሄደው ምድሪቱን በመያዝ፣ እዚያ የነበሩትን አሞራውያን አሳደዱአቸው፤ [40]ስለዚህ ሙሴ ገለዓድን የምናሴ ዘሮች ለሆኑት ለማኪራውያን ሰጣቸው፤ እነርሱም መኖሪያቸውን በዚያው አደረጉ:: [41]ከምናሴ ነገድ የሆነው ኢያዕር መኖሪያዎቻቸውን ወስዶ፣ "የኢያዕር መንደሮች" ብሎ ሰየማቸው:: [42]እንዲሁም ኖባህ ቄናትንና በዙሪያዋ ያሉትን መንደሮች በመያዝ በራሱ ስም፣ "ኖባህ" ብሎ ጠራቸው::

## እስራኤላውያን ከግብፅ እስከ ሞዓብ ሲጓዙ የሰፈሩባቸው ቦታዎች

**33** እስራኤላውያን በየነገዳቸው ተከፋፍለው በሙሴና በአሮን መሪነት ከግብፅ ወጥተው፣ በጒዞ ላይ ሳሉ የሰፈሩባቸው ቦታዎች እነዚህ ናቸው፤ [2]ሙሴም በጒዞአቸው ላይ ሳሉ የሰፈሩባቸውን ቦታዎች *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ትእዛዝ መዘገበ፤ በየቦታው እየሰፈሩ ያደረጉት ጒዞም ይህ ነው፤

[3]እስራኤላውያን በመጀመሪያው ወር በዐሥራ አምስተኛውም ቀን በፋሲካ ማግስት ከራምሴ ተነሡ፤ ግብፃውያን ሁሉ እያዩአቸውም በልበ ሙሉነት ተጓዙ:: [4]በዚህ ጊዜ ግብፃውያን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከመካከላቸው የገደላቸውን በኵሮቻቸውን ይቀብሩ ነበር፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በግብፅ አማልክት ላይ ፈርዶ ነበር::

[5]እስራኤላውያን ከራምሴ ተነሥተው በሱኮት ሰፈሩ::

[6]ከሱኮትም ተነሥተው በምድረ በዳው ዳርቻ በምትገኘው በኤታም ሰፈሩ::

[7]ከኤታም ተነሥተው ከበአልዛፎን በስተምሥራቅ ወዳለችው ወደ ፊሀሒሮት በመመለስ በሚግዶል አጠገብ ሰፈሩ::

[8]ከፊሀሒሮት* ተነሥተው በባሕሩ ውስጥ በማለፍ ወደ ምድረ በዳው ሄዱ፤ ከዚያም በኤታም ምድረ በዳ ሦስት ቀን ተጒዘው በማራ ሰፈሩ::

33፥6 ዘፀ13፥20 33፥7 ዘፀ14፥2:9 33፥8 ዘፀ14፥2: 22፤15፥23

*8 ብዙ የማሶሬቲክ፣ የኦሪተ ሳምራውያንና የቩልጌት ቅጆች *ከፊሀሒሮት ተነሥተው* የሚሉ ሲሆን፤ አያሌ የማሶሬቲክ ቅጆች ግን *ከፊሃሒሮት ፊት ለፊት ተነሥተው* ይላሉ::

32፥23 *ኀጢአታችሁ እንደሚያገኛችሁም ዕወቁ!* ድርድሩ ስሌታማ ሆኖአል፤ ይሁን እንጂ ቃላቸውን ባያከብሩ የሚያስከትልባቸውን በማመልከት ስምምነቱ ከከባድ ማስጠንቀቂያ ጋር ነበር::

32፥33 *ለምናሴ ነገድ እኩሌታ!* በዮርዳኖስ ማዶ ባለው አካባቢ ለመስፈር በቀረበው ጥያቄ ላይ ከሮቤልና ከጋድ ነገዶች ጋር ስምምነት እንደተደረገና የምናሴ ነገድ እኩሌታ አብረው እንዲሰፍሩ የተወሰነ ይመስላል::

*33፥1-49!* ከራምሴ ጀምሮ እስከ ሞዓብ ሜዳ ድረስ፣ በምድረ በዳ ጒዞ ወቅት እስራኤላውያን የሰፈሩባቸው በግልጽ የታወቁ አርባ የሚሆኑ አካባቢዎች ተዘርዝረዋል:: ነገር ግን ብዙዎቹ ቦታዎች በምድረ በዳው ጒዞ የሰፈራ ጣቢያዎች እንጂ፣ በከርስ ምድር የተገኘ በታሪካዊ ቅርስነት ለጥናት የሚቀርብ መረጃ የነበራቸው ከተሞች ባለመሆናቸው በትክክል ማመልከት አስቸጋሪ ነው:: ብዙዎቹ ቦታዎች (ቍ 19-29) ከዚህ ክፍል ሌላ በዘፀአትና በዘኍልቍ ውስጥ አልተጻፉም:: በሌላ ቦታ የተጠቀሱ አንዳንድ ቦታዎች ደግሞ (ለምሳሌ:- ተቤራ 11፥2፤ 21፥19 ይመ) በዚህ ክፍል አልተጻፈም:: መረጃው ቀጥሎ ያሉትን ድምዳሜዎች ያቀርባል፤ (1) ሙሴ የቦታዎችን ዝርዝር በእግዚአብሔር ትእዛዝ ጻፈ (ቍ 2)፤ (2) ብዙዎቹን ቦታዎች ማመልከት አስቸጋሪ ቢሆንም ዝርዝሩ የጒዞውን ሁኔታ የሚያሳይ ትክክለኛ የሆነ አጭር መግለጫ ተደርጎ መወሰድ አለበት፤ (3) ከራምሴ እስከ ሞዓብ ሜዳ ድረስ

[9]ከማራ ተነሥተው ዐሥራ ሁለት የውሃ ምንጮችና ሰባ የተምር ዛፎች ወደ ነበሩበት ወደ ኤሊም መጥተው በዚያ ሰፈሩ።
[10]ከኤሊም ተነሥተው በቀይ ባሕር* አጠገብ ሰፈሩ።
[11]ከቀይ ባሕር ተነሥተው በሲን ምድረ በዳ ሰፈሩ።
[12]ከሲን ምድረ በዳ ተነሥተው በራፍቃ ሰፈሩ።
[13]ከራፍቃ ተነሥተው በኤሉስ ሰፈሩ።
[14]ከኤሉስ ተነሥተው በራፊዲም ሰፈሩ፤ በዚያም ሕዝቡ የሚጠጣው ውሃ አልነበረም።
[15]ከራፊዲም ተነሥተው በሲና ምድረ በዳ ሰፈሩ።
[16]ከሲና ምድረ በዳ ተነሥተው በቂብሮት ሃታቫ ሰፈሩ።
[17]ከቂብሮት ሃታቫ ተነሥተው በሐጼሮት ሰፈሩ።
[18]ከሐጼሮት ተነሥተው በሪትማ ሰፈሩ።
[19]ከሪትማ ተነሥተው በሬሞን ዘፋሬስ ሰፈሩ።
[20]ከሬሞን ዘፋሬስ ተነሥተው በልብና ሰፈሩ።
[21]ከልብና ተነሥተው በሪሳ ሰፈሩ።
[22]ከሪሳ ተነሥተው በቀሄላታ ሰፈሩ።
[23]ከቀሄላታ ተነሥተው በሻፍር ተራራ ሰፈሩ።
[24]ከሻፍር ተራራ ተነሥተው በሐራዳ ሰፈሩ።
[25]ከሐራዳ ተነሥተው በመቅሄሎት ሰፈሩ።
[26]ከማቅሄሎት ተነሥተው በታሐት ሰፈሩ።
[27]ከታሐት ተነሥተው በታራ ሰፈሩ።
[28]ከታራ ተነሥተው በሚትቃ ሰፈሩ።
[29]ከሚትቃ ተነሥተው በሐሽሞና ሰፈሩ።
[30]ከሐሽሞና ተነሥተው በምሴሮት ሰፈሩ።
[31]ከምሴሮት ተነሥተው በብኔያዕቃን ሰፈሩ።
[32]ከብኔያዕቃን ተነሥተው በሖርሃጊድጋድ ሰፈሩ።
[33]ከሖርሃጊድጋድም ተነሥተው በዮጥባታ ሰፈሩ።
[34]ከዮጥባታ ተነሥተው በዔብሮና ሰፈሩ።
[35]ከዔብሮና ተነሥተው በዔጽዮንጋብር ሰፈሩ።
[36]ከዔጽዮንጋብር ተነሥተው በጺን ምድረ በዳ ባለችው በቃዴስ ሰፈሩ።
[37]ከቃዴስ ተነሥተው በኤዶም ዳርቻ ባለው በሖር ተራራ ሰፈሩ። [38]*በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ትእዛዝ ካህኑ አሮን ወደ ሖር ተራራ ወጣ፤ እዚያም እስራኤላውያን ከግብፅ በወጡ በአርባኛው ዓመት፣ በአምስተኛው ወር፣ ከወሩም በመጀመሪያው ቀን ሞተ። [39]አሮን በሖር ተራራ ላይ ሲሞት፣ ዕድሜው መቶ ሃያ ሦስት ዓመት ነበር።
[40]በከነዓን በምትገኘው በኔጌብ የሚኖረው ከነዓናዊው የዓራድ ንጉሥ፣ የእስራኤላውያንን መምጣት ሰማ።
[41]እነርሱም ከሖር ተራራ ተነሥተው በሴልሞና ሰፈሩ።
[42]ከሴልሞና ተነሥተው በፉኖን ሰፈሩ።
[43]ከፉኖን ተነሥተው በአቦት ሰፈሩ።
[44]ከአቦት ተነሥተው በሞዓብ ዳርቻ በምትገኘው በኢየአባሪም ሰፈሩ።
[45]ከኢይም ተነሥተው በዲቦንጋድ ሰፈሩ።
[46]ከዲቦንጋድ ተነሥተው በዓልሞንዲብላታይም ሰፈሩ።
[47]ከዓልሞንዲብላታይም ተነሥተው በናባው አጠገብ በሚገኙት በዓብሪም ተራራዎች ላይ ሰፈሩ።
[48]ከዓብሪም ተራራዎች ተነሥተው ከኢያሪኮ ማዶ በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ ባለው በሞዓብ ሜዳ ላይ ሰፈሩ።
[49]እዚያም በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ በሞዓብ ሜዳ ከቤት የሺሞት እስከ አቤልሰጢም ባለው ስፍራ ሰፈሩ።

[50]ከኢያሪኮ ማዶ በዮርዳኖስ አጠገብ ባለው በሞዓብ ሜዳ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [51]"እስራኤላውያንን ተናገራቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ 'ወደ ከነዓን ለመግባት ዮርዳኖስን ስትሻገሩ፣ [52]የምድሪቱን ነዋሪዎች በሙሉ ከፊታችሁ አሳዳችሁ አስወጧቸው፤ የተቀረጹ ምስሎቻቸውንና ቀልጠው የተሠሩ ጣዖቶቻቸውን በሙሉ አጥፉ፤ እንዲሁም በኰረብታ ላይ የተሠሩትን መስገጃዎቻቸውን ሁሉ አፈራርሱ። [53]ምድሪቱን ርስት አድርጌ ሰጥቻችኋለሁና ውረሷት፤ ኑሩባትም። [54]ምድሪቱንም በየጐሣዎቻችሁ በዕጣ ተከፋፈሉ። ከፍ ያለ ቍጥር ላለው ሰፋ ያለውን፣ ዝቅተኛ ቍጥር ላለው ደግሞ አነስተኛውን ስጡ፤ ምንም ይሁን ምን በዕጣ የወጣላቸው፣

*10 በዕብራይስጥ *ያም ሱፍ* የሚል ሲሆን፣ የደንገል ባሕር ማለት ነው።

33፥9 ዘፀ15፥27
33፥10 ዘፀ16፥1
33፥11 ዘፀ16፥1
33፥14 ዘፀ15፥22፤ 17፥2
33፥15 ዘፀ17፥1፤ 19፥1
33፥16 ዘኍ11፥34
33፥17 ዘኍ11፥35
33፥20 ኢሱ10፥29፤ 12፥15፤15፥42፤21፥13፤2ነገ8፥22፤19፥8፤23፥31፤1ዜና6፥57፤2ዜና21፥10፤ኢሳ37፥8፤ኤር52፥1
33፥30 ዘዳ10፥6
33፥31 ዘዳ10፥6
33፥33 ዘዳ10፥7
33፥35 ዘዳ2፥8፤ 1ነገ9፥26፤22፥48
33፥36 ዘኍ13፥21
33፥37 ዘፍ36፥16፤ ዘኍ20፥16፡22
33፥38 ዘፀ16፥35፤ ዘኍ20፥25-28፤ 27፥13
33፥40 ዘፍ10፥18፤ 12፥9፤ዘኍ21፥1
33፥43 ዘኍ21፥10
33፥44 ዘኍ21፥11
33፥47 ዘኍ27፥12፤ 32፥3
33፥48 ዘፍ13፥10፤ ዘኍ22፥1፤26፥3፤ 27፥12፤ኢሱ12፥9
33፥49 ዘኍ21፥16፤ ኢሱ12፥3፤13፥20፤ ሕዝ25፥9
33፥50 ቍ48
33፥51 ዘኍ34፥2፤ ኢሱ3፥17
33፥52 ዘሌ 26፥1፤ መዝ 106፥34-36
33፥53 ዘዳ11፥31፤ 17፥14፤ኢሱ1፥11፤ 21፥43
33፥54 ዘሌ16፥8፤ ዘኍ26፥54፤35፥8፤ 36፥2፤ኢሱ18፥10

ያሉት አርባ ቦታዎች የተራ ቍጥር አቀማመጥ ሁኔታ ዝርዝሩ የተወሰነ ስልት የተከተለ መሆኑን ያሳያል፤ ይህም ያልተጠቀሱትን ቦታዎች ለማወቅ ይረዳል። (4) በሙሴ የሕግ መጻሕፍት ውስጥ በተመለከተው የትውልድ ሐረግ ላይ እንደ ተጻፈው፣ ጥንት ትርጕም ያላቸውና አስፈላጊ የነበሩ ነገሮች ዛሬ ለእኛ ግልጽ ላይሆኑ ይችላሉ (5) በመሠረቱ ይህ ጽሑፍ በረጅሙ የምድረ በዳ ጕዞአቸው ወቅት ለሕዝቡ የሆነውን የእግዚአብሔርን በረከት የሚገልጽ ነው። እስራኤል በምድረ በዳ ጕዞ ያሳለፈውን ሁኔታ በመዘረዘሩ ከመልከዓ ምድር ጋር በተያያዘ አስፈላጊነቱ ባይካድም በይበልጥ ግን እግዚአብሔር ሕዝቡን ነጻ ማውጣቱን የሚገልጽ መንፈሳዊ ጽሑፍ ነው።

33፥52 *የምድሪቱን ነዋሪዎች በሙሉ ከፊታችሁ አሳዳችሁ አስወጧቸው፤ የተቀረጹ ምስሎቻቸውን.. አጥፉ፤* እስራኤላውያን ከምድያማውያን ጋር ጦርነት ባደረጉበት ጊዜ እንደ ፈጸሙት ሁሉ (ም 31)፣ በከነዓንም ሕዝብ ሁሉ ላይ ያደርጉ ዘንድ አስፈላጊ ነበር። የከነዓናውያን የጣዖት አምልኮ ሥርዐት ምልክት የሆኑትን ነገሮች ሁሉ ለማጥፋት የተሰጠው ትእዛዝ ከሁሉም ይልቅ ትኩረት የተሰጠው ነበር።

የራሳቸው ርስት ይሆናል። አከፋፈሉም በየአባቶቻችሁ ነገዶች አንጻር ይሁን።

[55] ‘የምድሪቱን ነዋሪዎች አሳዳችሁ ሳታስወጧቸው ብትቀሩ ግን፣ እንዲኖሩ የተዋችኋቸው ሰዎች ለዐይናችሁ ስንጥር፣ ለጐናችሁም እሾኽ ይሆኑባችኋል፤ በምትኖሩበትም ምድር ችግር ይፈጥሩባችኋል። [56] እኔም በእነርሱ ላይ ለማድረግ ያሰብሁትን በእናንተ ላይ አደርግባችኋለሁ።’ ”

## የከነዓን አዋሳኞች

**34** እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2] “እስራኤላውያንን እዘዛቸው፤ እንዲህም በላቸው፤ ‘ርስት አድርጋችሁ በዕጣ ወደምትካፈሏት ወደ ከነዓን ምድር በምትገቡበት ጊዜ አዋሳኞቿ እነዚህ ይሆናሉ፤

[3] ‘የደቡብ ድንበራችሁ በኤዶም ወሰን ላይ ካለው ከጺን ምድረ በዳ ጥቂቱን ይጨምራል፤ በምሥራቅም በኩል የደቡብ ድንበራችሁ ከጨው ባሕር[a] ጫፍ ይጀምርና [4] በአቅረቢም መተላለፊያ አቋርጦ እስከ ጺን ይሄድና በስተ ደቡብ እስከ ቃዴስ በርኔ ይዘልቃል፤ ከዚያም በሐጸር አዳር ዐልፎ እስከ ዓጽሞን ይደርስና [5] ዞሮ ከግብፅ ወንዝ ደረቅ መደብ ጋር በመገናኘት መጨረሻው ባሕሩ[b] ይሆናል።

[6] ‘የምዕራቡ ድንበራችሁ ደግሞ የታላቁ ባሕር ጠረፍ ይሆናል። በምዕራቡ በኩል ያለው ወሰናችሁም ይኸው ነው።

[7] ‘የሰሜን ድንበራችሁን ከታላቁ ባሕር እስከ ሖር ተራራ ምልክት አድርጉበት፤ [8] ከሖር ተራራ እስከ ሌቦሐማት[c] እንደዚሁ አድርጉ፤ ከዚያም ወሰኑ እስከ ጽዳድ ይሄድና [9] እስከ ዚፍሮን በመቀጠል መጨረሻው ሐጻርዔናን ይሆናል፤ በሰሜን በኩል ያለው ወሰናችሁ ይኸው ነው።

[10] ‘ለምሥራቁ ድንበራችሁም እንደዚሁ ከሐጻርዔናን እስከ ሴፋማ ምልክት አድርጉበት። [11] ወሰኑም ከሴፋማ እንሥቶ ከዓይን በስተ ምሥራቅ እስካለው እስከ ሪብላ ቍልቍል ይወርድና ከኪኔሬት ባሕር[d] በስተ ምሥራቅ እስካሉት ሸንተረሮች ድረስ ይዘልቃል። [12] ከዚያም ወሰኑ የዮርዳኖስን ወንዝ ተከትሎ መጨረሻው የጨው ባሕር ይሆናል።

“ ‘እንግዲህ በዙሪያዋ ካሉት ወሰኖቿ ጋር ምድራችሁ ይህች ናት።’ ”

[13] ሙሴ እስራኤላውያንን እንዲህ ብሎ አዘዛቸው፤ “ይህችን ምድር ርስት አድርጋችሁ በዕጣ ተካፈሉ፤ እግዚአብሔርም (ያህዌ) ለዘጠኙና ለግማሹ ነገድ እንድትሰጥ አዞአል፤ [14] የሮቤል ነገድ ቤተ ሰቦች፣ የጋድ ነገድ ቤተ ሰቦች እንዲሁም የምናሴ ነገድ እኩሌታ ርስታቸውን ተቀብለዋልና። [15] እነዚህ ሁለቱ ነገዶችና እኩሌታው ነገድ ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ፣ ከኢያሪኮ ማዶ በፀሓይ መውጫ በኩል ርስታቸውን ተቀብለዋል።”

[16] እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [17] “ምድሪቱን ርስት አድርገው የሚያከፋፍሏችሁ ካህኑ አልዓዛርና የነዌ ልጅ ኢያሱ ናቸው፤ [18] ምድሪቱን በማከፋፈሉ እንዲረዱም ከየነገዱ አንዳንድ መሪ ውሰዱ። [19] ስማቸውም ይህ ነው፤

ከይሁዳ ነገድ፣
የዮፎኒ ልጅ ካሌብ፤
[20] ከስምዖን ነገድ፣
የዓሚሁድ ልጅ ሰላሚኤል፤
[21] ከብንያም ነገድ፣
የኪስሎን ልጅ ኤልዳድ፤
[22] የዳን ነገድ መሪ፣
የዮግሊ ልጅ ቡቂ፤
[23] የዮሴፍ ልጅ የምናሴ ነገድ መሪ፣
የሱፊድ ልጅ አኒኤል፤
[24] የዮሴፍ ልጅ የኤፍሬም ነገድ መሪ፣
የሺፍጣን ልጅ ቀሙኤል፤
[25] የዛብሎን ነገድ መሪ፣
የፌርናክ ልጅ ኤሊሳፈን፤
[26] የይሳኮር ነገድ መሪ፣
የዖዛ ልጅ ፈልጢኤል፤
[27] የአሴር ነገድ መሪ፣
የሴሎሚ ልጅ አሒሁድ፤
[28] የንፍታሌም ነገድ መሪ፣
የዓሚሁድ ልጅ ፈዳሄል።”

[29] እነዚህ በከነዓን ምድር ለእስራኤላውያን ርስት እንዲያከፋፍሉ እግዚአብሔር (ያህዌ) ያዘዛቸው ሰዎች ናቸው።

## ለሌዋውያን የተሰጡ ከተሞች

**35** ከኢያሪኮ[a] ማዶ በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ፣ በሞዓብ ሜዳ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [2] “ከሚወርሱት ርስት ላይ ለሌዋውያን የሚኖሩባቸውን ከተሞች እንዲሰጧቸው እስራኤላውያንን እዘዛቸው፤ በየከተሞቹ ዙሪያም የግጦሽ መሬት ስጧቸው። [3] ከተሞቹ ለእነርሱ መኖሪያ፣ የግጦሽ መሬቱ ለከብቶቻቸው፣ ለበግና ለፍየል

33፥55 ኢሱ23፥13፤ መሳ2፥3፤መዝ106፥36፤ኢሳ55፥13፤ሕዝ2፥6፤28፥24፤ሚክ7፥4፤2ቆሮ12፥7
33፥56 ዘኍ14፥28
34፥1 ዘፍ17፥8፤2፤ ዘኍ33፥51፤ዘዳ1፥7-8፤ኢሱ23፥4፤መዝ78፥54-55፤105፥11፤ ሕዝ47፥15
34፥3 ዘፍ14፥3፤ዘኍ13፥21፤ ኢሱ15፥1-3
34፥4 ዘኍ32፥8፤ኢሱ15፥3፡4፤መሳ1፥36
34፥5 ዘፍ15፥18
34፥6 ኢሱ1፥4፤9፥1፤15፥12፡47፤23፥4፤ ሕዝ47፥10፡15፡19-20፤48፥28
34፥7 ሕዝ47፥15-17፤ዘኍ 20፥22
34፥8 ዘኍ13፥21፤ ኢሱ13፥5
34፥10 ኢሱ 15፥5
34፥11 ዘዳ3፥17፤ ኢሱ11፥2፤13፥27፤15፥32፤21፥16፤2ነገ23፥33፤25፥6፡21፤1ዜና4፥32፤ኤር39፥5፤52፥9፡27
34፥13 ዘሌ16፥8፤ ኢሱ13፥6፤18፥10፤14፥1-5፤ኢሳ49፥8፤65፥9፤ሕዝ45፥1፤ሚክ2፥5
34፥14 ዘኍ32፥19፤ ዘዳ33፥21፤ኢሱ14፥3
34፥17 ዘኍ11፥28፤ ዘዳ 1፥38
34፥18 ዘኍ1፥4፤ ኢሱ14፥1
34፥19 ቍ29፤ዘፍ29፥35፤ዘኍ26፥65፤ ዘዳ33፥7፤መዝ60፥7
34፥20 ዘፍ29፥33
34፥21 ዘፍ49፥27፤ መሳ5፥14፤መዝ68፥27
34፥23 ዘኍ1፥34
34፥24 ዘኍ1፥32
34፥25 ዘፍ30፥20
34፥27 ዘኍ1፥40
34፥29 ቍ19
35፥1 ዘኍ22፥1
35፥2 ዘሌ25፥32-34፤ኢሱ14፥3፡4፤21፥1-42
35፥3 ዘዳ18፥6፤ ኢሱ14፥4፤21፥2

[a]3 ሙት ባሕር ነው።
[b]5 የሜድትራኒያን ባሕር ነው።
[c]8 ወይም እስከ ሌቦሐማት መግቢያ ድረስ
[d]11 የገሊላ ባሕር ማለት ነው።
[a]1 በዕብራይስጥ የኢያሪኮ ዮርዳኖስ ማለት ሲሆን፣ ይህም የዮርዳኖስ ወንዝ የጥንት ስም ሳይሆን አይቀርም።

*34፥3-12፤* አራቱን የከነዓን ዳርቻዎች በዝርዝር ማመልከቱ ለመረጃ ያህል ብቻ ሳይሆን እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሰጠው ስጦታ ምን ያህል ሰፊ እንደ ሆነም ለመግለጽ ነው።

*34፥13-15፤* ይህም የሮቤልና የጋድ እንዲሁም የምናሴ ነገድ እኩሌታ በዮርዳኖስ ማዶ በመስፈሩ (ም 32 ይመ) የተፈጠረ አዲስ ሁኔታ ነው።

*34፥16-29፤* የየነገዱ አለቃ የሆኑትን የአዲሶቹን ሰዎች ስም መዘርዘሩ በመጀመሪያው ትውልድ አለቃ የነበሩትን ሰዎች ስም የመዘርዘር ሁኔታን ያስታውሳል (1፥5-16)፤ አሁን ግን የተሰጠው ተስፋ አስተማማኝነቱ ግልጽ ሆኖ ይታያል፤ አዲሶቹ የነገድ መሪዎች መሬት በማከፋፈል አልዓዛርንና ኢያሱን ይረዳሉ።

*35፥1-5፤* ሌዋውያን ከሌሎች ነገዶች ጋር ርስትን ስለማይወርሱ (1፥47-53) ለራሳቸውና ለቤተ ሰቦቻቸው መኖሪያ እንዲሁም ለከብቶቻቸው ማስማሪያ የሚሆን ከተማ ማግኘት ስለሚኖርባቸው ይኸውም በአንድ ለየት ባለ አካባቢ እንዲሰፍሩ ሳይሆን፣ በተለያየ አቅጣጫ በምድሪቱ ሁሉ እንዲቀመጡ ማድረግ አስፈላጊ ነበር። ይህ ትእዛዝ ተግባራዊ መሆኑን በኢሱ 21 ላይ ተመልክቶአል።

መንጎቻቸውና ለሌሎቹም እንስሶቻቸው ይሆናሉ።

[4]“በየከተሞቹ ዙሪያ ለሌዋውያኑ የምትሰጧቸውም የግጦሽ መሬት ከከተማው ቅጥር አንድ ሺህ ክንድ[*] ይዘረጋል። [5]ከዚያም ከተማውን መካከል በማድረግ ወደ ምሥራቅ ሁለት ሺህ ክንድ፣[**] ወደ ደቡብ ሁለት ሺህ ክንድ፣ ወደ ምዕራብ ሁለት ሺህ ክንድ፣ ወደ ሰሜን ሁለት ሺህ ክንድ ከከተማው ውጭ ለካ፤ እነዚህንም ቦታዎች ለከተሞቹ የግጦሽ መሬት ያደርጓቸዋል።

## የመማጸኛ ከተሞች

35፥6-34 ማመ - ዘዳ 4፥41-43፤ 19፥1-14፤ ኢሱ 20፥1-9

[6]“ለሌዋውያኑ ከምትሰጧቸው ከተሞች ስድስቱ፣ ሰው የገደለ ሸሽቶ የሚጠጋባቸው መማጸኛ ከተሞች ይሆናሉ፤ በተጨማሪም አርባ ሁለት ከተሞች ስጧቸው፤ [7]የግጦሽ መሬቶቻቸውን ጨምሮ በጠቅላላው አርባ ስምንት ከተሞች ለሌዋውያኑ ስጧቸው። [8]እስራኤላውያን ከወረሷት ምድር ላይ ለሌዋውያኑ የምትሰጧቸው ከተሞች እያንዳንዱ ነገድ እንዳለው ድርሻ መጠን ይሆናል። ብዙ ካለው ነገድ ላይ ብዙ ከተሞች እንዲሁም ጥቂት ካለው ነገድ ላይ ጥቂት ከተሞችን ውሰዱ።”

[9]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [10]“እስራኤላውያንን እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ ‘ወደ ከነዓን ለመግባት ዮርዳኖስን በምትሻገሩበት ጊዜ፣ [11]ሳያስበው ሰው የገደለ ሰው ሸሽቶ የሚጠጋባቸው ከተሞች እንዲሆኑ መማጸኛ ከተሞችን ምረጡ። [12]እነዚህም፣ ነፍሰ ገዳዩ በማኅበሩ ዘንድ ለፍርድ ከመቅረቡ በፊት እንዳይሞት ከደም ተበቃዩ የሚሸሸባቸው የመማጸኛ ከተሞች ይሆናሉ። [13]እነዚህ ለሌዋውያኑ የምትሰጧቸው ስድስት ከተሞች መማጸኛ ከተሞቻችሁ ይሆናሉ። [14]ስለዚህ ከዮርዳኖስ ወዲህ ሦስቱን እንዲሁም በከነዓን ሦስቱን የመማጸኛ ከተሞች አድርጋችሁ ስጡ። [15]እነዚህም ስድስት ከተሞች ሳያስበው ሰው የገደለ ማንኛውም ሰው እንዲሸሸባቸው ለእስራኤላውያን፣ ለመጻተኞችና በመካከላቸው ለሚኖር ለማንኛውም ሕዝብ የመማጸኛ ቦታዎች ይሆናሉ።

[16]“ ‘አንድ ሰው ሌላውን እንዲሞት በብረት ቢመታው ነፍሰ ገዳይ ነው፤ በሞትም ይቀጣል። [17]ወይም አንድ ሰው መግደል የሚችል ድንጋይ በእጁ ቢይዝና ሌላውን ሰው እንዲሞት ቢመታው ነፍሰ ገዳይ ነው፤ በሞትም ይቀጣል። [18]ወይም አንድ ሰው መግደል የሚችል ዕንጨት በእጁ ቢይዝና ሌላውን ሰው እንዲሞት ቢመታው ነፍሰ ገዳይ ነው፤ በሞትም ይቀጣል። [19]ደም መላሹም ነፍሰ ገዳዩን ይግደለው፤ ባገኘውም ጊዜ ይግደለው። [20]አንድ ሰው አስቦበት ሌላውን በክፋት ገፍትሮ ቢጥለው ወይም እንዲሞት ሆን ብሎ አንዳች ነገር ቢወረውርበት [21]ወይም ደግሞ በጥላቻ ተነሣሥቶ በእጁ ቢመታውና ቢሞት፣ ያ ሰው በሞት ይቀጣል፤ ነፍሰ ገዳይ

35፥5፤ ዘሌ 25፥34፤ ኢሱ 3፥42ዜና 11፥14፤ 13፥9፤23፥2፤31፥19
35፥6 ቊ 11፤ኢሱ 21፥13
35፥8 ዘኍ 26፥54፤ 33፥54
35፥10 ዘኍ 33፥51፤ ዘዳ 9፥1፤ኢሱ 1፥2፡11
35፥11 ቊ 22-25፤ ዘፀ 21፥13
35፥12 ቊ 19፡24፡ 25፡26፡27፡28፤ዘዳ 19፥6፤ኢሱ 20፥3፤ 2ሳሙ 14፥11
35፥13 ቊ 6፡14
35፥16 ዘፀ 21፥12
35፥19 ቊ 12፡21
35፥20 ዘፀ 21፥14
35፥21 ቊ 19፤ ዘፀ 21፥14

[*]4 አራት መቶ አምሳ ሜትር ያህል ነው።
[**]5 ዘጠኝ መቶ ሜትር ያህል ነው።

*35፥6-15፤* ስድስት የሌዋውያን ከተሞች በምድሪቱ አስፈላጊ በሆኑ ቦታዎች ላይ እንዲመሠረቱ ተደርጉአል፤ ከእነዚህም ሦስቱ በዮርዳኖስ ማዶ፣ ሦስቱ ደግሞ በከነዓን ምድር የነበሩ ሲሆን፣ በድንገት የነፍስ ግድያ የፈጸመ ሰው ከሚደርስበት በቀል ለማምለጥ አመቺ የሆኑ መሸሸጊያና መማጸኛ ከተሞች ነበሩ። በኢሱ 20 ላይ ለዚህ ዐላማ ስለተመረጡት ቦታዎች ተገልጾአል።

*35፥16-21፤* ሆን ተብሎ ስለሚፈጸም የነፍስ ግድያ የተለያየ ገለጻ ቀርቦአል።

## የመማፀኛ ከተሞች

ከፍተኛ ለሆነ ወንጀል የመማፀኛ ከተሞችን የማዘጋጀት ሐሳብ በቀልን ለመፈጸም በሚያስችለው በልማዳዊው የነገዶች ሕግ እና ፍትሕን በተከተለውና በብዙዎች ዘንድ ተቀባይነት በሚኖረው በወንጀለኛ መቅጫ ሕግ መካከል ባለው ውጥረት ላይ የተመሠረተ ሥር የሰደደ ጉዳይ ነው።

በሥጋ ዝምድና የሚደረጉ ግጭቶች ብዙውን ጊዜ ከዘላን ኅብረተሰብ ጋር የተያያዘ ነው። እስራኤል በአንድ አካባቢ/ሰፍራ ወደ መከተም ሂደት ውስጥ ያለ ኅብረተሰብ እንደ መሆኑ ወንጀለኛ ያልሆኑ ሰዎች ፍርድ ፊት ሳይቀርቡና ሳይረጋገጥ እንዳይገደሉ ለማድረግ መካከለኛ የሆነ እርምጃ መውሰዱ አስፈላጊ ነበር። ከነፍስ ገዳይነት ነጻ መውጣት የሚቻለው በአገሩ ማኅበር ነጻ ማውጣት እና በዘመኑ ያለው ሊቀ ካህን ከሞተ ብቻ ነው።



ነው፤ ደም መላሹም ገዳዩን ባገኘው ጊዜ ይግደለው።

[22]“ ‘ነገር ግን በጥላቻ ሳይሆን እንዲያው በድንገት አንዱ ሌላውን ገፍትሮ ቢጥለው ወይም ሳያስበው አንዳች ነገር ቢወረውርበት [23]ወይም መግደል የሚችል ድንጋይ ሳያይ ጥሎበት ቢሞት፣ ጠላቱ ስላልሆነና ሊጐዳውም አስቦ ያላደረገው ስለ ሆነ፣ [24]ማኅበሩ በዚህ ሰውና በደመኛው መካከል በእነዚህ ደንቦች መሠረት ይፍረድ። [25]ማኅበሩም በነፍስ ገዳይነት የተከሰሰውን ሰው ከደመኛው እጅ በማስጣል ወደ ሸሸበት ወደ መማጸኛው ከተማ ይመልሰው፤ የተቀደሰ ዘይት የተቀባው ሊቀ ካህን እስኪሞትም ድረስ በዚያ ይቈይ።

[26]“ ‘ሆኖም ተከሳሹ ሰው ሸሽቶ ከተጠጋበት መማጸኛ ከተማ ክልል ከወጣ፣ [27]ደም ተበቃዩም ከከተማው ውጭ ካገኘው፣ ተከሳሹን ሊገድለው ይችላል፤ በነፍስ ገዳይነትም አይጠየቅም። [28]ተከሳሹም ሊቀ ካህናቱ እስኪሞት ድረስ በመማጸኛው ከተማ ይቈይ፤ ወደ ገዛ ርስቱ መመለስ የሚችለው ከሊቀ ካህናቱ ሞት በኋላ ብቻ ነው።

[29]“ ‘እንግዲህ በየትኛውም በምትኖሩበት ስፍራ፣ በሚመጡት ትውልዶች ሁሉ የምትፈጽሟቸው ሕጋዊ ግዴታዎቻችሁ እነዚህ ናቸው።

[30]“ ‘ሰው የገደለ ማንኛውም ሰው በሞት የሚቀጣው ምስክሮች ሲመሰክሩበት ብቻ ነው፤ ይሁን እንጂ ማንም ሰው በአንድ ምስክር ብቻ በሞት አይቀጣም።

[31]“ ‘በሞት መቀጣት ስላለበት ሰው የነፍስ ዋጋ አትቀበሉ፤ ፈጽሞ መሞት አለበት።

[32]“ ‘ወደ መማጸኛ ከተማ ሸሽቶ ስለ ገባ ስለ ማንኛውም ሰው የደም ዋጋ በመቀበል ሊቀ ካህናቱ ከመሞቱ በፊት ወደ አገሩ ተመልሶ ሄዶ እዚያ እንዲኖር አታድርጉ።

[33]“ ‘ደም ምድሪቱን ስለሚያረክሳት፣ ደም ለፈሰሰባትም ምድር ስርየት ሊደረግላት የሚችለው በሌላ ሳይሆን በዚያው ደሙን ባፈሰሰው ሰው ደም ብቻ በመሆኑ፣ የምትኖሩባትን ምድር በደም አታርክሷት፤ [34]የምትኖሩባትን፣ እኔም የማድርባትን ምድር አታርክሷት እኔ እግዚአብሔር (ያህዌ) በእስራኤላውያን መካከል እኖራለሁና።’ ”

35፥22 ዘፀ21፥13
35፥24 ቍ12
35፥25 ቍ32፤ ዘፀ28፥41፤29፥7
35፥29 ዘኍ10፥8፤ 27፥11፤ዘፀ12፥20
35፥30 ዘዳ17፥6፤ 19፥15፤ማቴ18፥16፤ ዮሐ7፥51
35፥31 ዘፀ21፥30፤ ኢዮ6፥22፤መዝ 49፥8፤ምሳ13፥8
35፥33 ዘፍ4፥10
35፥34 ዘሌ18፥24፡ 25፤ዘፀ29፥45

## የሰለጰዓድ ሴት ልጆች ርስት

36፥1-12 ተጓ ምብ - ዘኍ 27፥1-11

**36** ከዮሴፍ ዘርያ ጐሣዎች የሆኑ የምናሴ ልጅ፣ የማኪር ልጅ፣ የገለዓድ ጐሣ የቤተ ሰብ አለቆች ወደ ሙሴና የእስራኤላውያን ቤተ ሰቦች አለቆች ወደ ሆኑት መሪዎች ቀርበው ተናገሩ፤ [2]እንዲህም አሉ፤ “ምድሪቱን በዕጣ ከፋፍለህ ለእስራኤላውያን ርስት አድርገህ እንድትሰጣቸው እግዚአብሔር (ያህዌ) አንተን ጌታዬን ባዘዘ ጊዜ የወንድማችንን የሰለጰዓድን ድርሻ ለሴቶች ልጆቹ እንድትሰጥ አዞሃል። [3]ከሌሎች የእስራኤል ነገዶች ባል ቢያገቡ ድርሻቸው ከእኛ የዘር ርስት ላይ ተወስዶ የሚያገቧቸው ሰዎች ላሉበት ነገድ ይተላለፋል፤ ይህ ከሆነ ደግሞ በዕጣ ከተደለደለልን ርስት ላይ ከፊሉ ሊቀነስብን ነው። [4]የእስራኤላውያን ዓመተ ኢዮቤልዩ በሚመጣበት ጊዜ የእነርሱ ድርሻ ወደ ባሎቻቸው ነገድ ይጨመራል፤ ይህ ከሆነም ድርሻቸው ከአባቶቻችን ነገድ ርስት ላይ ይወሰዳል።”

[5]ከዚህ በኋላ ሙሴ እግዚአብሔር (ያህዌ) በተናገረው መሠረት እስራኤላውያንን እንዲህ ሲል አዘዛቸው፤ “የዮሴፍ ነገድ የተናገረው ትክክል ነው፤ [6]እንግዲህ የሰለጰዓድን ሴት ልጆች በተመለከተ እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚያዝዘው ይህ ነው፤ ከአባታቸው ነገድ ወገን እስከ ሆነ ድረስ የወደዱትን ማግባት ይችላሉ። [7]እያንዳንዱ እስራኤላዊም ከቀደሙት አባቶቹ በወረሰው ርስት ይጽና፤ በእስራኤል ከአንዱ ነገድ ወደ ሌላው ነገድ የሚተላለፍ ርስት አይኖርም። [8]እያንዳንዱ እስራኤላዊ የየአባቶቹን ርስት መውረስ ስላለበት፣ በማንኛውም የእስራኤል ነገድ ውስጥ ርስት የምትወርስ የትኛዪቱም ሴት፣ ከአባቷ ነገድ ወገን የሆነውን አንዱን ማግባት አለባት። [9]እያንዳንዱ የእስራኤል ነገድ የወረሰውን መሬት እንዳለ ማቈየት ስላለበት፣ ርስት ከአንዱ ነገድ ወደ ሌላው ነገድ አይተላለፍም።”

[10]ስለዚህም የሰለጰዓድ ሴት ልጆች እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዳዘዘው አደረጉ። [11]የሰለጰዓድ ሴት ልጆች፤ ማህለህ፣ ቲርጻ፣ ዔግላ፣ ሚልካ፣ ኑዓ ከአባታቸው ወንድሞች ልጆች ጋር ተጋቡ። [12]ከዮሴፍ ልጅ ከምናሴ ዘርያ ጐሣዎች ጋር በመጋባታቸው፣ ርስታቸው በዚያው በአባታቸው ጐሣና ነገድ እጅ

36፥1 ዘፍ50፥23፤ ዘኍ26፥28፡30፥27፥2
36፥2 ዘኍ26፥33፤ 33፥54
36፥4 ዘሌ25፥10
36፥7 ዘሌ25፥23
36፥8 1ዜና23፥22
36፥11 ዘኍ26፥33
36፥12 1ዜና7፥15

35፥22 *በጥላቻ ሳይሆን፤* እነዚህ መሸሸጊያ ከተሞች በድንገት የነፍስ ግድያን ለሚፈጽም ሰው ተገን ይሆኑ ዘንድ ለመማጸኛነት የተቈረቈሩ ናቸው።

35፥24 *በእነዚህ ደንቦች መሠረት፤* በምሕረት የሚደረግ ማንኛውም ነገር የሚያስነቅፍ ነው። በዚህ ምክንያት በድንገት የነፍስ ግድያን የፈጸመ ሰው ጒዳዩ በዳኛ መወሰን አለበት። በተጨማሪም ዋናው ካህን እስኪሞት ድረስ ተከሳሹ በመሸሸጊያው ከተማ እንዲቈይ ይደረግ ነበር፤ ነገር ግን ተከሳሹ ከመሸሸጊያው ከተማ ወጥቶ በደም ተበቃዩ ቢገደል አይጠየቅበትም።

*35፥25-28፤* የኢሱ 20፥6 ማብ ይመ።

35፥30 *ምስክሮች፤* ጥፋተኛ ያልሆነው ወገን ያለ በቂ ማስረጃ እንዳይከሰስና የሞት ፍርድ እንዳይፈረድበት ለመከላከል ነው።

*35፥32፤* በድንገት የነፍስ ግድያ የፈጸመ ሰው እንኳ፣ የነፍስ ዋጋ በመክፈል ከመሸሸጊያ ከተማ መውጣት አይችልም ነበር።

35፥33 *ደም ምድሪቱን ስለሚያረክሳት፤* ነፍስ መግደል የሕይወትን ቅድስና ብቻ ሳይሆን የተቀደሰውንም የእግዚአብሔር ምድር የሚያረክስ ነው።

*36፥1-13፤* ይህ ክፍል የሰለጰዓድ ሴት ልጆችን ታሪክ በመቀጠል ደስ የሚያሰኝና ሰፋ ያለ ሐሳብ ይዟል (27፥1-11 ይመ)። ሴቶቹ ልጆች የአባታቸውን ርስት እንዲወርሱ እግዚአብሔር ለሙሴ ከሰጠው ትእዛዝ አንጻር ተጨማሪ ጥያቄዎች የቀረቡ ሲሆን፣ ይኸውም እነዚህ ሴቶች ልጆች ከነገዳቸው ውጭ ባል ቢያገቡ የቤተ ሰቡ ርስት እንዴት ይደረጋል? የመጀመሪያው ስጦታ መሠረታዊ ዐላማ አይደናቀፍም ወይ? የሚሉ ጥያቄዎች ናቸው። እነዚህ ጥያቄዎች በመቅረባቸው የቤተ ሰቡ ርስት “ከአንድ ነገድ ወደ ሌላ ነገድ” (ቍ 9) እንዳይተላለፍ፣ እያንዳንዱ ከነገዱ ሳይወጣ ጋብቻ እንዲፈጽም ውሳኔ ተደረገ።

እንዳለ ቀረ።

[13]ከኢያሪኮ[ሠ] ማዶ፣ በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ፣ በሞዓብ ሜዳ ሳሉ እግዚአብሔር (ያህዌ) በሙሴ አማካይነት ለእስራኤላውያን

36፥13 ዘሌ7፥38፤ 27፥34፤ዘኍ22፥1

የሰጣቸው ትእዛዞችና ደንቦች እነዚህ ናቸው።

[ሠ]13 በዕብራይስጥ *የኢያሪኮ ዮርዳኖስ* የሚል ሲሆን፣ ይህም የዮርዳኖስ ወንዝ የጥንት ስም ሳይሆን አይቀርም።

36፥10 *የሰለጰዓድ ሴት ልጆች እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘ አደረጉ፤* የእግዚአብሔርን ጸጋ በመቃወምና ፈቃዱንም ችላ በማለት ብዙ ጊዜ የእግዚአብሔር ሕዝብ ያደረገውን ዐመፅ የሚናገረው የዘኍልቍ መጽሐፍ ደስ የሚል አጭር ጽሑፍ በማቅረብ ታሪኩን ይደመድማል። ስለ አባታቸው ስምና በምድሪቱ ስለ አለው ርስታቸው የተቈረቈሩት እነዚህ የተከበሩ ሴቶች ልጆች እግዚአብሔርን ታዘዋል።

# ኦሪት ዘዳግም

## መግቢያ

**አሰያየሙ**

"ዘዳግም" የሚለው ቃል፣ 'ድጋሚ' የሚል ትርጉም ሲኖረው፣ ቀደም ባሉት የኦሪት መጻሕፍት የተጻፉትን ሕግጋት ጠቅለል አድርጎ በድጋሚ የሚያቀርብ መጽሐፍ ነው።

**ጸሐፊው**

ሙሴ የመጽሐፉ ጸሐፊ እንደሆነ በዚሁ መጽሐፍ በብዙ ስፍራዎች ላይ ተጠቅሶ ይገኛል (1፥5፤ 31፥9፡22፡24)። ሙሴ ከሞተ በኋላ ያለውን ግን (ም 34) ሌላ ሰው እንደጻፈው ይገመታል። ኢየሱስም ሆነ የአዲስ ኪዳን ጸሐፊዎች መጽሐፉ በሙሴ እንደተጻፈ መስክረዋል (ማቴ19፥7-8፤ ማር10፥3-5፤ ዮሐ5፥46-47፤ ሐሥ3፥22-23፤ 7፥37-38፤ ሮሜ10፥19)። በተጨማሪም ኢየሱስ ከዘዳግም መጽሐፍ በመጥቀስ ቃሉ ሥልጣናዊ መሆኑን ሲያረጋግጥ (ማቴ4፥4፡7፡10)፣ በአዲስ ኪዳን ከሙቶ የማያንሱ ጥቅሶችና ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ የተጠቀሱ ሐሳቦች ከዘዳግም መጽሐፍ ተወስደዋል፤ ትውፊትም ይህ መጽሐፍ በሙሴ እንደተጻፈ ይመሰክራል (ማር12፥19ይመ)። የኦሪት ዘፍጥረትን መግቢያ ይመ።

**የተጻፈበት ጊዜ**

የዘዳግም መጽሐፍ 1406 ዓ.ቅ.ክ ላይ እንደተጻፈ ይገመታል። የኦሪት ዘፍጥረትን መግቢያ ይመ።

**ታሪካዊ መቼቱ**

ይህ መጽሐፍ ሙሴና እስራኤላውያን፣ በሞዓብ ምድር የዮርዳኖስ ወንዝ ወደ ሙት ባሕር በሚፈስበት አካባቢ መስፈራቸውን ያመለክታል (1፥5)። ሙሴ መሪነቱን ለኢያሱ በሚያስተላልፍበት ወቅት፣ የእስራኤል ሕዝብ ወደ ከነዓን ምድር ለመግባት እንዲዘጋጁ የሚያደርግ የስንብት ንግግር ያቀርባል። ይህ የስንብት ቃል እንደገና ኪዳኑን እንዲያስታውሱ የቀረበ ሲሆን፣ በዚህ ወቅት ሙሴ ሕጉን አበክሮ መናገሩ ተገቢ ነበር። ኦሪት ዘዳግም ከሌሎቹ የኦሪት መጻሕፍት በተለየ መንገድ ከትረካ ይልቅ የስብከት አቀራረብ ያለው የሙሴ ማስገንዘቢያ ነው ማለት ይቻላል።

**ትምህርተ መለኮቱ**

መጽሐፉ የእግዚአብሔርን ሉዓላዊነት እንዲሁም እግዚአብሔር ለሕዝቡና ሕዝቡም ለእግዚአብሔር ያለውን የፍቅር ግንኙነት በሰፋት ይተርካል። የዘዳግም መጽሐፍ መንፈሳዊ ትኩረቱ እንዲሁም በአምልኮና በመታዘዝ ሙሉ በሙሉ ለእግዚአብሔር መሰጠትን በተመለከተ የሚያስተምረው ትምህርት ለተቀሩት የብሉይና የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ፋና ወጊ እንዲሆን አድርጎታል።

**ሥነ ጽሑፋዊ ውቅሩ**

የዘዳግም የጽሑፍ ታሪካዊ ውቅር፣ ታሪካዊ መቼቱን የሚደግፍ ነው። ገላጭ መሆኑ፣ ድግግሞሹ፣ ያለፈውን በድጋሚ ማቅረቡ እንዲሁም ቅርጽየለሽ አቀራረቡ የጊዜን ቅደም ተከተል ሳይጠብቅ መጻፉን ያመለክታሉ (ለምሳሌ 10፥3 ይመ)። በአጠቃላይ መጽሐፉ በእግዚአብሔርና በሕዝቡ መካከል ያለውን ኪዳን በግልጽ ማሳየቱ ("የብሉይ ኪዳን ታላላቅ ኪዳናት" የሚለውን ሰንጠረዥ በገጽ 18 ላይ ይመ)፣ የኪዳኑን መታደስ የሚገልጽ ሰነድ ነው ማለት ይቻላል።

**አስተዋፅኦ**

1. መግቢያ (1፥1-5)
2. ታሪካዊ መቅድም (1፥6-4፥43)
3. የኪዳኑ ቅድመ ሁኔታ (4፥44-26፥19)
   - ሀ. ታላቁ ትእዛዝ – ፍጹም መገዛትን ይጠይቃል (4፥44-11፥32)
   - ለ. ንዑሳን ትእዛዛት (ም 12-26)
     1. የመቀደስ ሥርዐት (12፥1-16፥17)
     2. የአገር መሪዎችና ጻድቅ ሕዝብ (16፥18-21፥21)
     3. የእግዚአብሔር መንግሥት ቅድስና (21፥22-25፥19)
     4. የእግዚአብሔርን አዳኝነትና ንጉሥነት መመስከር (ም 26)
4. የመርገምና የበረከት አይቀሬነት (ም 27-30)
5. በኪዳኑ መሠረት መሪን መተካት (ም 31-34)
   - ሀ የአመራር ለውጥ (31፥1-29)
   - ለ የሙሴ መዝሙር (31፥30-32፥47)
   - ሐ ሙሴና የእስራኤል ነገዶች የበረከት ኪዳን (32፥48-33፥29)
   - መ የሙሴ መሞትና የኢያሱ መተካት (ም 34)

**አንዳንድ ጊዜ የዘዳግም መጽሐፍ ተደራስያኑን በሦስት ይከፍላል**

የመጀመሪያው (1፥1-4፥43)
ሁለተኛው ክፍል (4፥44-28፥68)
ሦስተኛው ክፍል (ም 29-33)
የሙሴ መሞት (ም 34)

## እስራኤል ከኮሬብ እንዲነሡ የተሰጠ ትእዛዝ

**1** ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ ዓረባ በተባለው ምድረ በዳ ከሱጳ ትይዩ፣ በፋራንና በጦፌል፣ በላባን፣ በሐጼሮትና በዲዛሃብ መካከል ሳሉ፣ ሙሴ ለእስራኤል ሁሉ የተናገረው ቃል ይህ ነው:: [2](በሴይር ተራራ መንገድ ከኮሬብ እስከ ቃዴስ በርኔ ዐሥራ አንድ ቀን ያስሄዳል::)

[3]በአርባኛው ዓመት፣ በዐሥራ አንደኛው ወር ከወሩም በመጀመሪያው ቀን እስራኤላውያንን በሚመለከት *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ያዘዘውን ሁሉ ሙሴ ለእነርሱ ነገራቸው:: [4]ይህ የሆነው በሐሴቦን ይገዛ የነበረውን የአሞራውያንን ንጉሥ ሴዎንና በአስታሮት ይገዛ የነበረውን የዐግን ንጉሥ ባሳንን በኤድራይ ድል ካደረገ በኋላ ነው::

[5]ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ በሞዓብ ምድር ሳሉ፣ ሙሴ ይህን ሕግ እንዲህ እያለ መግለጥ ጀመረ፤

[6]"*እግዚአብሔር* አምላካችን (ያህዌ ኤሎሂም) በኮሬብ እንዲህ አለን፤ 'እነሆ በዚህ ተራራ ለረጅም ጊዜ ቈይታችኋል:: [7]ሰፈር ነቅላችሁ ወደ ኰረብታማው የአሞራውያን አገር ጕዞ ቀጥሉ፤ ከዚያም በዓረባ፣ በተራሮቹ፣ በምዕራብ ኰረብታዎች ግርጌ፣ በኔጌብና በባሕሩ ዳርቻ ወዳሉት አጐራባች ሕዝቦች ሁሉ ሂዱ፤ እንዲሁም ወደ ከነዓናውያን ምድርና ወደ ሊባኖስ፣ እስከ ታላቁ ወንዝ እስከ ኤፍራጥስ ድረስ ዝለቁ:: [8]እነሆ፤ ይህችን ምድር ሰጥቻችኋለሁ፤ እንግዲህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለአባቶቻችሁ ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ ከእነርሱም በኋላ ለዘሮቻቸው ሊሰጥ የማለላቸውን ምድር ገብታችሁ ውረሱ::"

### የመሪዎች መሾም

[9]"እኔም በዚያን ጊዜ እንዲህ አልኋችሁ፤ ብቻዬን ልሸከማችሁ አልችልም፤ [10]*አምላካችሁ እግዚአብሔር* (ያህዌ ኤሎሂም) ቍጥራችሁን ጨምሮአል፤ ስለዚህ ዛሬ እናንተ እንደ ሰማይ ከዋክብት በዝታችኋል:: [11]አሁንም የአባቶቻችሁ *አምላክ እግዚአብሔር* (ያህዌ ኤሎሂም) ሺህ ጊዜ ያብዛችሁ፤ በሰጠውም ተስፋ መሠረት ይባርካችሁ! [12]ይሁን እንጂ ችግራችሁን፣ ሸክማችሁንና ክርክራችሁን ሁሉ ብቻዬን እንዴት አድርጌ መሸከም እችላለሁ? [13]ጥበበኞችን፣ አስተዋዮችንና የተከበሩ ሰዎችን ከየነገዳችሁ ምረጡ፤ እኔም በእናንተ ላይ እሾማቸዋለሁ::"

[14]እናንተም፣ "ይደረግ ዘንድ ያቀረብኸው ሐሳብ መልካም ነው" ብላችሁ መለሳችሁልኝ::

[15]ስለዚህ እኔም የየነገዶቻችሁን አለቆች ጥበበኞችንና የተከበሩትን ሰዎች ተቀብዬ፣ ሻለቆች፣ መቶ አለቆች፣ አምሳ አለቆችና ዐሥር አለቆች እንዲሁም የየነገዱ ሹማምንት በማድረግ በእናንተ ላይ ሥልጣን እንዲኖራቸው ሾምኋቸው:: [16]በዚያን ጊዜም ዳኞቻችሁን እንዲህ ስል አዘዝኋቸው፤ "በወንድሞቻችሁ መካከል የሚነሣውን ክርክር ያለ አድልዎ እዩት፤ ሙግቱ ወንድማማች በሆኑ እስራኤላውያን መካከል ወይም በአንድ እስራኤላዊና በመጻተኛ መካከል ቢሆን፣ በትክክል ፍረዱ:: [17]በፍርድ አድልዎ አታድርጉ፤ ትልቁንም ትንሹንም እኩል እዩ፤ ፍርድ የእግዚአብሔር ስለሆነ፣ ማንኛውንም ሰው አትፍሩ:: ከዐቅማችሁ በላይ የሆነውን ሁሉ ወደ እኔ አምጡት፤ እኔ እየዋለሁ::" [18]በዚያን ጊዜ ማድረግ የነበረባችሁን ሁሉ ነገርኋችሁ::

1፥1 ቍ7፤ዘኍ10፥12፤ 13፥29፤ዘዳ2፥8፤3፥17፤ 4፥46፤ኢሱ3፥16፤ 8፥14፤11፥2፤ሕዝ47፥8
1፥2 ቍ19፤ ዘፍ14፥7፤ዘፀ3፥1፤ ዘኍ24፥18፤ዘዳ2፥14፤ 9፥23፤ኢሱ15፥3
1፥3 ዘፍ50፥3፤ ዘኍ14፥33፤32፥13፤ ዘዳ4፥1-2፤8፥2፤ 34፥8፤ኢሱ4፥19፤ ዕብ3፥7-9፤
1፥4 ዘፍ10፥16፤ 14፥7፤ዘኍ21፥21-26፤21፥33-35፤ ዘዳ3፥10፤ኢሱ9፥10፤ 12፥4፤1ዜና11፥44
1፥5 ዘኍ21፥11
1፥6 ዘፀ3፥1፤ ዘኍ10፥13፤ዘዳ2፥3
1፥7 ቍ1፤19፤ ዘፍ2፥14፤10፥18፤ ዘኍ21፥1፤ዘዳ2፥24፤ 7፥1፤11፥24፤ ኢሱ10፥5፤11፥16፤ 12፥8፤2ሳሙ24፥7፤
1፥8 ዘፀ13፥11፤ ዘኍ14፥23፤34፥2፤ ኢሱ23፥13፤ ዕብ6፥13-14
1፥9 ዘፀ18፥18፤ ዘኍ11፥14፤ መዝ38፥4
1፥10 ቍ11፤ ዘፍ15፥5፤22፥17፤ ዘኍ10፥36፤ዘዳ7፥13 ፤ኢሳ51፥2፤60፥22፤ ሕዝ16፥7፤33፥24
1፥11 ቍ8፤10፤ ዘፀ32፥13፤2ሳሙ 24፥3፤1ዜና21፥3
1፥12 ዘፀ 5፥22፤18፥18
1፥13 ዘፍ47፥6
1፥15 ዘፍ47፥6፤ዘፀ 5፥14፤18፥25፤ዘኍ1፥ 4፤11፥16፤31፥14፤ ኢሱ1፥10፤3፥2፤1ሳሙ8፥12፤22፥7፤1ነገ14፥27
1፥16 ዘፍ31፥37፤ ዘፀ12፥19፡49፤22፥21፤1ነገ3፥9፤መዝ72፥1፤ዮሐ7፥24
1፥17 ዘፀ18፥16፡26፤ዘሌ19፥15፤ምሳ29፥25፤ሐሥ10፥34፤ያዕ 2፥1
1፥18 ዘፍ39፥11

---

*1፥1-5፤ መግቢያው የመጽሐፉን አጠቃላይ ታሪካዊ ዳራ ይናገራል::*

1፥1 *ዓረባ፤* ከገሊላ ባሕር ጀምሮ እስከ ሙት ባሕር ደቡባዊ ጫፍ ድረስ ያለውን የዮርዳኖስን ሸለቆ እንዲሁም እስከ አካባ ባሕረ ሰላጤ ድረስ ያለውን ሸለቆ የሚያጠቃልል ስፍራ ነው:: *ሱጳ ... ፋራን... ጦፌል... ላባን ... ሐጼሮት ... ዲዛሃብ፤* ከሲና እስከ ሞዓብ ምድር ባለው መንገድ ላይ የሚገኙ ቦታዎች ናቸው:: *ሙሴ ... የተናገረው፤* በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ የምናገኛቸው ቃሎች በሙሉ፣ እስራኤላውያን የዮርዳኖስን ወንዝ ከመሻገራቸው በፊት፣ ሙሴ ወደ ሕይወቱ ፍጻሜ ገደማ የተናገራቸው ቃሎች ናቸው ማለት ይቻላል::

1፥2 *ኮሬብ፤* በ33፥2 ላይ ከተጠቀሰው በስተቀር በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ለሲና ተራራ የተሰጠ ስም ነው:: *ቃዴስ በርኔ፤* የዘፍ 14፥7 ማብ ይመ:: *ሴይር፤* የዘፍ 36፥8 ማብ ይመ::

1፥3 *አርባኛው ዓመት፤* ከግብፅ ምድር ከወጡ በኋላ ማለት ነው:: እግዚአብሔር እስራኤላውያን በሲና ምድረበዳ ለ40 ዓመታት ያህል በማንከራተት ቀጥቶአቸዋል፤ የቀጣቸውም ወደ ከነዓን ሲገቡ በቃዴስ ባርኔ ባዛቸው መሠረት ስላልገቡ ነው (ዘኍ 14፥33-34):: ይህ 40 ዓመት በሲና ያሳለፉትን ጊዜና ወደ ቃዴስ ያደረጉትን ጕዞ እንዲሁም ከዚያ በኋላ በምድረ በዳው የፈጁትን ሠላሳ ስምንት ዓመት ሁሉ የሚያጠቃልል ነው (2፥14 ፤ 8፥2-5፤ 29፥5-6፤ ዘኍ 14፥29-35፤ 32፥13 ዕብ 3፥7-19 ይመ):: *ዐሥራ አንደኛው ወር፤* ከጥር እስከ የካቲት ማለት ነው::

1፥5 *ይህን ሕግ፤* በሲና ተራራ የተሰጡትን እንዲሁም በዘፀ 20-24 በዘሌዋውያንና በዘኍልቍ መጻሕፍት ተመዝግበው የሚገኙትን ዐሥሩን ትእዛዛትና ሌሎቹንም ሕግጋት ማለት ነው:: በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ የምናገኛቸው ሕግጋት እጥር ምጥን ብለው ቀርበዋል፤ ትርጕማቸው ተፍታቶ ተሰጥቶአል፤ ደግሞም እስራኤላውያን በከነዓን ምድር ሲኖሩ ሊያጋጥማቸው ከሚችል አዲስና ልዩ ሁኔታ ጋር ተገናዝቦአል:: እንግዲህ የዘዳግም መጽሐፍ የቃል ኪዳኑ ሕግ የታደሰበት ማለትም ከጊዜው ሁኔታ ጋር የተገናዘበበት መዝገብ ነው ማለት ይቻላል::

*1፥7፤* ኢሱ 1፥4 ይመ:: ምድሪቱ በተለያዩ መልክዐ ምድራዊ አቀማመጦች ተገልጸለች:: *ዓረባ፤* የቍ 1 ማብ ይመ፤ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ግን የዮርዳኖስ ወንዝ የሚገኝበት ሸለቆና የሙት ባሕር ያለበትን አካባቢ ለማመልከት ብቻ ነው:: *ተራሮቹ፤* ከሰሜን እስከ ደቡብ ያለው መሃል አገር ማለት ነው:: *በምዕራብ ኰረብታዎች ግርጌ፤* ወደ ሚድትራኒያን ባሕር የሚያሽቈለቍል አካባቢ ማለት ነው:: *ኔጌብ፤* የዘፍ 12፥9 ማብ ይመ:: *በባሕሩ ዳርቻ፤* በሜድትራኒያን ባሕር ጠረፍ ዳር ዳሩን የሚገኘው ምድር ማለት ነው:: "የከነዓናውያን ምድር" እንዲሁም፣ "... ሊባኖስ፣ እስከ ታላቁ ወንዝ እስከ ኤፍራጥስ" የሚለው ሰሜናዊውን ክፍል ያመለክታል:: "ኰረብታማው የአሞራውያን አገር" የሚለው ባጠቃላይ በመካከለኛውና በስተ ደቡብ በኩል የሚገኙትን ተራራማ ስፍራዎች ያመለክታል:: ስለ ምድሪቱ የተሰጠው ገለጻ፣ በዘፍ 15፥18-21 ላይ ለአብርሃም ከተሰጠው የተስፋ ቃል (ቍ 8)፣ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ደግሞ ለይስሐቅ ዘሮች ከተሰጠው የተስፋ ቃል (ዘፍ 26፥2-4) እንዲሁም ውሎ አድሮ ለያዕቆብ ዘሮች ከተሰጠው የተስፋ ቃል (ዘፍ 35፥11-12) ጋር ይስማማል::

*1፥9-18፤* ከ16፥18-20፤ ከዘፀ 18፥13-26 ጋር ያነጻጽሩ::

1፥10 *አምላካችሁ እግዚአብሔር፤* ይህ መጠሪያ ስም በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶአል:: እንደ ሰማይ ከዋክብት፤ 10፥22፤ 28፥62፤ ዘፍ 13፥16 እና ማብ 15፥5 እና ማብ፤ 22፥17፤ 26፥4፤ ዘፀ 32፥13 ይመ::

## የሰላዮች መላክ

[19]ከዚያም አምላካችን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ባዘዘን መሠረት ከኮሬብ ተነሥተን እንዳያ ችሁት በዚያ ጭልጥ ባለና በሚያስፈራ ምድረ በዳ ዐልፈን፣ በኰረብታማው በአሞራውያን አገር በኩል ወደ ቃዴስ በርኔ መጣን። [20]እኔም፣ እንዲህ አልኋችሁ፤ "*አምላካችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጠን ወደ ኰረብታ ማው የአሞራውያን አገር ደርሳችኋል፤ [21]እነሆ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ምድሪቱን ሰጥቶአችኋል፤ አሁንም የአባቶቻችሁ *አምላክ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በነገራችሁ መሠረት ውጡ፤ ውረ ሷትም፤ አትፍሩ፤ አትደንግጡም።"

[22]ከዚያም ሁላችሁ ወደ እኔ መጥታችሁ፣ "ምድሪቱን እንዲሰልሉልን ሰዎች አስቀድመን እንላክ፤ እነርሱም ወደዚያ የሚያደርሰንን መን ገድና የምንሄድባቸውን ከተሞች በማጥናት ተመልሰው ይነግሩናል" አላችሁ።

[23]ይህም ሐሳብ መልካም መስሎ ታየኝ፤ እኔም ከእያንዳንዱ ነገድ አንዳንድ ሰው በማድረግ ከእናንተ ዐሥራ ሁለት ሰዎች መረጥሁ። [24]እነርሱም ተነሥተው ወደ ኰረብታማው አገር ከወጡ በኋላ ወደ ኤሽኮል ሸለቆ መጥተው ምድሪቱን ሰለሉ። [25]ከምድሪቱም ፍሬ ወደ እኛ ይዘው በመምጣት፣ "*አምላካችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚሰጠን ምድር መልካም ናት" ብለው ነገሩን።

## በእግዚአብሔር ላይ ማመፅ

[26]እናንተ ግን ለመውጣት ፈቃደኞች አልነ በራችሁም፤ *በአምላካችን* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዝ ላይ ዐመፃችሁ። [27]በየድንኳኖቻችሁ ሆናችሁ እንዲህ ስትሉ አጕረመረማችሁ፤ "*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጠልቶናል፤ ስለዚህም ከግብፅ ያወጣን አሞራውያን እንዲያጠፉን፣ በእጃቸው አሳልፎ ሊሰጠን ነው። [28]ታዲያ ወዴት መሄድ እንችላለን? ወንድሞቻችን፣ 'ሰዎቹ ከእኛ ይልቅ ብርቱዎችና ቁመተ ረጃጅሞች፣ ከተሞቹም ትልልቆችና እስከ ሰማይ በሚደርስ ቅጥር የታጠሩ ናቸው፤ እንዲያውም በዚያ የዔናቅን ልጆች አይተናቸዋል' ሲሉ እንድንፈራ አድርገውናል።"

[29]እኔም አልኋችሁ፤ "አትሸበሩ፤ አትፍሯ ቸውም። [30]በፊታችሁ የሚሄደው *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከዚህ በፊት ዐይናችሁ እያየ በግብፅ እንዳደረገላችሁ ሁሉ፣ አሁንም ለእናንተ ይዋጋል፤ [31]በምድረ በዳው እንደ አደ ረገው ሁሉ። በዚያም አባት ልጁን እንደሚ ሸከም፣ እናንተን *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እዚህ ስፍራ እስክትደርሱ በመጣች ሁባት መንገድ ሁሉ እንዴት እንደ ተሸከማችሁ አይታችኋል።"

[32]ይህም ሆኖ *በአምላካችሁ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አልታመናችሁም፤ [33]በጕዞ ላይ ሳላችሁ የምትሰፍሩባቸውን ቦታዎች ለመፈ ለግና የምትሄዱበትን መንገድ ለማሳየት እርሱ ሌሊት በእሳት፣ ቀን በደመና ይመ ራችሁ ነበር።

[34]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) እናንተ ያላችሁትን በሰማ ጊዜ ተቈጣ፤ ማለም፤ [35]"ለቀደሙት አባ ቶቻችሁ ለመስጠት የማልሁላቸውን መልካሚ ቱን ምድር፣ ከዚህ ክፉ ትውልድ አንድም ሰው አያያትም፤ [36]ከዮፎኒ ልጅ ከካሌብ በስተ ቀር የሚያያት የለም፤ እርሱ ያያታል፤ *እግዚ አብሔርን* (ያህዌ) በፍጹም ልቡ ስለ ተከተለ፣ የረገ ጣትን ምድር ለእርሱና ለዘሮቹ እሰጣለሁ።"

[37]በእናንተ ምክንያት *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እኔን ተቈጥቶ እንዲህ አለኝ፤ "አንተም ብትሆን አትገባባትም። [38]ረዳትህ የነዌ ልጅ ኢያሱ ግን ይገባባታል፤ ምድሪቱን እንዲ ወርሱ እስራኤልን የሚመራ እርሱ ስለ ሆነ፣ አበረታታው። [39]ይማረካሉ ያላችኋቸው ታናና ሾች፣ ክፉና በጎውን ለይተው የማያውቁት ልጆቻችሁ ምድሪቱን ይገቡባታል፤ ለእነርሱም እሰጣቸዋለሁ፤ እነርሱም ይወርሷታል። [40]እና ንተ ግን፣ ተመልሳችሁ ወደ ቀይ ባሕር[ሀ] የሚወስደውን መንገድ ይዛችሁ ወደ ምድረ በዳው ተጓዙ።"

[41]እናንተ፣ "*እግዚአብሔርን* (ያህዌ) በድለናል፤ *አምላ ካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባዘዘንም መሠረት

[ሀ]40 ዕብራይስጡ፣ *ያም ሳውፍ* ይለዋል፤ ይኸውም፣ የደንገል ባሕር ማለት ነው።

1፥19 ቍ.2፡7፤ ዘኍ13፥26፤ዘዳ2፥7፤ 8፥15፤32፥10፤ መዝ136፥16፤ ኤር2፥2፡6፤ሆሴ13፥5
1፥21 ዘኍ14፥9፤ ዘዳ7፥18፤9፥23፤ ኢያ1፥6፡9፡18፤8፥1፤ 10፥8፤24ሙ-10፥12፤ መዝ27፥14፤ ኢሳ8፥1፤10፥8
1፥22 ዘፍ42፥9፤ ዘኍ13፥1-3
1፥23 ዘኍ13፥1-3
1፥24 ዘኍ13፥21-25፤32፥9
1፥25 ዘኍ13፥27፤1 4፥7፤ኢያ1፥2
1፥26 ዘኍ14፥1-4፡9
1፥27 ዘዳ9፥28፤ መዝ106፥25
1፥28 ዘኍ13፥32፡ 33፤ዘዳ9፥1-3
1፥29 ዘዳ3፥22፤ 7፥18፤ 20፥1፡3፤ 31፥6፤ነሀ4፥14
1፥30 ዘፀ14፥14
1፥31 ዘፀ19፥4፤ ዘዳ32፥10-12፤ መዝ28፥9፤ኢሳ46፥3-4፤ 63፥9፤ኤር31፥32፤ ሆሴ11፥3፤ሐሥ13፥18፤
1፥32 ዘኍ14፥11፤ ዘዳ9፥23፤መዝ78፥22 ፤106፥24፤ሶፎ3፥2፤ ዕብ3፥19፤ይሁዳ1፥5
1፥33 ዘፀ13፥21፤ ዘኍ9፥15-23፤ 10፥33፤ ነህ9፥12፤መዝ78፥14፤
1፥34 ዘኍ11፥1፤ 32፥14፤14፥23፡28-30፤ ሕዝ20፥15፤ዕብ3፥11
1፥35 ዘኍ14፥29
1፥36 ዘኍ13፥6፤ 14፥24
1፥37 ዘኍ27፥13፤ መዝ106፥32
1፥38 ዘኍ11፥28፤ ዘዳ3፥28፤31፥7፤ ኢያ11፥23፤ መዝ78፥55፤136፥21
1፥39 ዘኍ14፥31 ኢሳ7፥15-16
1፥40 ዘፀ14፥27፤ መሳ11፥16

*1፥19-46፤* ዘኍ 13፥14 ይመ።

1፥21 *እግዚአብሔር በነገራችሁ መሠረት፤* ስለ ተስፋዪቱ ምድር የተሰጠው የተስፋ ቃል (የቍ 7 ማብ ይመ)፣ በሚገነደው ቀጥቋጦ አጠ ገብ ለሙሴ እንደገና ተረጋግጦለታል (ቍ 8፤ ዘፀ 3፥8፡17)። አሁን ደግሞ እስራኤላውያን ወደ ምድሪቱ ገብተው እንዲወርሱአት ተነገራቸው። *አትፍሩ አትደንግጡም፤* 31፥8፤ ኢያ 1፥9፤ 8፥1፤ 10፥25 ይመ።

1፥23 *ዐሥራ ሁለት፤* ስማቸው በዘኍ 13፥4-15 ላይ በዝርዝር ተጠቅሶአል።

1፥24 *ኤሽኮል፤* የቃሉ ትርጕም 'ስብስብ' እንደ ማለት ነው።

1፥26 *ዐመፃችሁ፤* በዚህ ወቅት የነበሩት ሰዎች ባያምፁም፣ ቀደም ሲል ከነበረው ዐመፀኛ ትውልድ ጋር እንደ ተባበረ ሕዝብ ተቈጥረዋል (5፥2 ይመ፤ ከ29፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥27 *አጕረመረማችሁ፤* የዘፀ 15፥24 ማብ ይመ። *እግዚአብ ሔር ጠልቶናል፤* ከዘዳግም መጽሐፍ መሪ ሐሳብ አንጻር ሲታይ የሕዝቡ አነጋገር ምፀታዊ ነው (መግቢያ፤ ትምህርተ መለኮት የሚለውን ይመ)።

1፥28 *የዔናቅን ልጆች፤* ቀድሞ በከነዓን ምድር ይኖሩ የነበሩና ብርቱ ሕዝብ ተብሎ የተነገረላቸው ናቸው (2፥10፡21፤ 9፥2፤ ዘኍ 13፥32 ይመ)።

1፥30 *በግብፅ እንዳደረገላችሁ፤* ዘፀ 14፥1-15፥19 ይመ።

1፥31 *እግዚአብሔር ... ተሸከማችሁ፤* የኢሳ 41፥10፡13፤ 43፥1-2 ማብ ይመ፤ ከኢሳ 40፥11፤ ኤር 31፥10፤ ሕዝ 34፥11-16 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥33 *ሌሊት በእሳት፣ ቀን በደመና፤* የእግዚአብሔር ሀልዎት እስራኤላውያንን በመንገዳቸው ሊመራ በመገናኛው ድንኳን ዐናት ላይ በሰፈፈው ደመና ውስጥ ነበር (ዘፀ 13፥21 እና ማብ፤ 40፥34-38 ይመ)።

1፥36 *ካሌብ፤* ዘኍ 13፥30-14፥38፤ ኢያ 14፥6-15 ይመ።

1፥37 *በእናንተ ምክንያት፤* 3፥26፤ 4፥21 ይመ። ሙሴ ጥሩ ባልሆነ መንፈስ ተነሣሥቶ በመሪባ ውሃ ለማፍለቅ ዐለቱን በመታ ጊዜ፣ እግዚአብሔር ሙሴን ተቈጣው (ዘኍ 20፥9-13፤ 27፥12-14)። ሙሴን ለዚህ ኀጢአት የዳረጉት ራሳቸው እስራ ኤላውያን በመሆናቸው፣ እግዚአብሔር እነርሱንም ተቈጣቸው። ይህ ሁኔት (ቍ 37) የተፈጸመው ከፍ ሲል ባሉት ቍጥሮች ላይ የተጻፈው ታሪክ (ቍ 34-36) ከተፈጸመ ከ40 ዓመታት በኋላ ነው፤ ነገር ግን ሙሴ የእስራኤላውያንና የራሱን ኀጢአት ሊናገር ስለፈለገ፣ ሁለቱን ሁኔቶች አንድ ላይ አቅርቦአቸዋል።

1፥39 *ክፉውና በጎውን ለይተው የማያውቁት፤* የዘፍ 2፥9፤ የኢሳ 7፥15 ማብ ይመ።

1፥41 *እናንተም፤* የቍ 26 ማብ ይመ።

ወጥተን እንዋጋለን ብላችሁ መለሳችሁልኝ፡፡ ወደ ተራራማው አገር መሄድ ቀላል መስሎ ስለ ታያችሁ፣ እያንዳንዳችሁ የጦር መሣሪያችሁን ታጥቃችሁ ተነሣችሁ፡፡

[42]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ግን፣ "እኔ ከእናንተ ጋር አልሆንምና ወጥታችሁ እንዳትዋጉ፤ በጠላቶቻችሁ ድል ትነሣላችሁ ብለህ ንገራቸው" አለኝ፡፡

[43]እኔም ነገርኋችሁ፤ እናንተ ግን አላዳመጣችሁም፤ *በእግዚአብሔር* (በያህዌ) ትእዛዝ ላይ ዐምፃችሁ፤ በትዕቢታችሁ ወደ ኰረብታማዪቱ አገር ዘመታችሁ፡፡ [44]በነዚያ ኰረብቶች ላይ የሚኖሩት አሞራውያን ሊወጓችሁ ወጡ፤ እንደ ንብ ሰራዊትም ሆነው አባረሯችሁ፤ ከሴይር አንሥቶ እስከ ሔርማ ድረስ አሳደው መቷችሁ፡፡ [45]እናንተም ተመልሳችሁ መጥታችሁ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት አለቀሳችሁ፤ ነገር ግን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ልቅሶአችሁን አልሰማም፤ አላዳመጣችሁምም፡፡ [46]ስለዚህ ያን ያህል ጊዜ በማጥፋት በቃዴስ ብዙ ቀን ቈያችሁ፡፡

## በምድረ በዳ መንከራተት

**2** ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ባዘዘኝ መሠረት ተመለስን፤ ቀይ ባሕርን^ ይዘን ወደ ምድረ በዳው ተጓዝን፤ በሴይር ኰረብታማ አገር ዙሪያ ለረጅም ጊዜ ተንከራተትን፡፡

[2]ከዚያም እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲህ አለኝ፤ [3]"በዚህ በኰረብታማ አገር ዙሪያ እስኪበቃችሁ ተንከራታችኋል፤ አሁን ግን ወደ ሰሜን ተመለሱ፡፡ [4]ለሕዝቡም እነዚህን ትእዛዞች ስጣቸው፤ ሴይር በሚኖሩት በወንድሞቻችሁ በዔሳው ዘሮች ግዛት ዐልፋችሁ ትሄዳላችሁ፤ እነርሱ ይፈሯችኋል፤ ቢሆንም ከፍ ያለ ጥንቃቄ አድርጉ፡፡ [5]ከየትኛውም ምድራቸው ላይ ለጫማችሁ መርገጫ ታህል እንኳ መሬት ስለማልሰጣችሁ፣ ለጦርነት አታነሣሷቸው፡፡ ኰረብታማውን የሴይርን አገር ርስት አድርጌ ለዔሳው ሰጥቼዋለሁ፡፡ [6]ከዚያ ለምትበሉት ምግብም ሆነ ለምትጠጡት ውሃ በጥሬ ብር ትከፍሏቸዋላችሁ፡፡"

[7]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጃችሁ ሥራ ሁሉ ባርኮአችኋል፤ በዚህ ጭልጥ ባለው ምድረ በዳ ባደረጋችሁት ጕዞ ጠብቆአችኋል፡፡ በእነዚህ አርባ ዓመታት እግዚአብሔር ከእናንተ ጋር ነበርና አንዳችም ነገር አላጣችሁም፡፡

[8]ስለዚህ በሴይር የሚኖሩ የዔሳው ዘሮች የሆኑ ወንድሞቻችንን ዐልፈናቸው ሄድን፡፡ ከኤላትና ከጽዮንጋብር ከሚመጣው ከዓረባ መንገድ ተመልሰን፣ በሞአብ ምድረ በዳ መንገድ ተጓዝን፡፡

[9]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ)፣ "ከሞዓባውያን ምድር አንዳችም መሬት ስለማልሰጣችሁ አታስቸግሯቸው፤ ለጦርነትም አታነሣሷቸው፤ ዔርን ለሎጥ ዘሮች ርስት አድርጌ ሰጥቻቸዋለሁ" አለኝ፡፡

[10]በዚያም ጠንካራና ቍጥራቸው የበዛ እንዲሁም እንደ ዔናቃውያን ረጃጅም የሆኑ ኤሚማውያን ይኖሩ ነበር፡፡ [11]እነዚህም እንደ ዔናቃውያን ሁሉ ራፋይማውያን ናቸው ተብለው ይገመቱ ነበር፤ ሞዓባውያን ግን ኤሚማውያን ብለው ይጠሯቸዋል፡፡ [12]ሖራውያን ቀድሞ በሴይር ይኖሩ ነበር፤ የዔሳው ዘሮች ግን ከዚያ አሳደው አስወጧቸው፡፡ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ርስት አድርጎ በሰጠው ምድር ላይ እስራኤል እንዳደረገው ሁሉ፣ እነዚህም ሖራውያንን ከፊታቸው አጥፍተው መኖሪያቸውን እዚያው አደረጉ፡፡

[13]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) "አሁኑኑ ተነሡና የዘሬድን ደረቅ ወንዝ ተሻገሩ" አለን፤ እኛም ወንዙን ተሻገርን፡፡

[14]ቃዴስ በርኔን ከለቀቅንበት ጊዜ አንሥቶ የዘሬድን ደረቅ ወንዝ እስከ ተሻገርንበት ጊዜ ድረስ ሠላሳ ስምንት ዓመት ዐለፈ፡፡ በዚያን ጊዜም ለጦርነት ብቁ የሆኑት የዚያ ትውልድ ወንዶች ሁሉ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ስለ እነርሱ አስቀድሞ በማለው መሠረት ከሰፈሩ ፈጽመው ዐለቁ፡፡ [15]ከሰፈር ፈጽሞ እስኪያጠፋቸውም

^2 ዕብራይስጡ፣ ያም ሳውፍ ይለዋል፤ ይኸውም የደንገል ባሕር ማለት ነው፡፡

1፥42 ዘኍ14፥41-43
1፥44 ዘኍ14፥45፤ 24፥18፤መዝ118፥12
1፥45 ዘኍ14፥1፤ ኢዮ27፥9፤35፥13፤ መዝ18፥41፤28፥1፤ 39፥12፤66፥18፤ ምሳ1፥28፤28፥9፤ ኢሳ1፥15፤ኤር14፥12፤ ሰቆ3፥8፤ሚክ3፥4፤ ዮሐ9፥31
1፥46 ዘኍ20፥1
2፥1 ዘፀ14፥27፤ ዘኍ21፥4፤24፥18
2፥3 ዘዳ1፥6
2፥4 ቍ1፤ዘፍ36፥8፤ ዘፀ15፥16፤ ዘኍ20፥14-21፤ ዘዳ15፥16
2፥5 ኢሱ24፥4
2፥7 ቍ14፤ ዘፀ13፥21፤ ዘኍ14፥33፤ 32፥13፤ዘዳ1፥19፤ 8፥2-4፤ኢሱ5፥6፤ ነህ9፥21፤አሞ2፥10
2፥8 ዘኍ20፥21፤ 21፥4፤ 33፥35፤ ዘዳ1፥1፤1ነገ9፥26
2፥9 ዘፍ19፥38፤ ዘኍ21፥15፤መዝ83፥8
2፥10 ዘፍ14፥5፤ ዘኍ13፥22:33
2፥11 ዘፍ14፥5
2፥12 ዘፍ14፥6፤ ዘኍ21፥25:35
2፥13 ዘኍ21፥12
2፥14 ቍ7፤ ዘኍ14፥29-35፤ ዘዳ1፥2፤1፥34-35፤ ኢሱ5፥6
2፥15 መዝ106፥26፤ ይሁዳ1፥5

1፥43 *እናንተ ግን ... በእግዚአብሔር ትእዛዝ ላይ ዐመፃችሁ፤* በቍ 26 ላይ ከቀረበባቸው ክስ ጋር አንድ ዐይነት ነው፡፡ በመጀመሪያ ሕዝቡ ወደ ምድሪቱ ለመግባት አሻፈረኝ ብለው በእግዚአብሔር ትእዛዝ ላይ ዐመፁ፤ ከዚያም ወደ ምድሪቱ ዘልቀን አንገባም በማለት ዐመፁ፡፡ ከመጀመሪያው ዐመፃቸው በኋላ እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር ሊወጣ አልፈለገም፤ የእርሱ አብሮ መሆን እጅግ አስፈላጊ በመሆኑ፣ እስራኤል ይህንን እውነት መማር ነበረባቸው፡፡

1፥44 *ንብ፤* የዘፀ 23፥28 ማብ ይመ፡፡

1፥45 *በእግዚአብሔር ፊት፤* በማደሪያው ድንኳን ፊት ማለት ነው፡፡

*2፥1-3፥11፤* ዘኍ 20፥14-21፥35 ይመ፡፡

2፥1 *ቀይ ባሕር፤* ምናልባት የአካባ ባሕረ ሰላጤ ሊሆን ይችላል (የ1ነገ 9፥26 ማብ ይመ)፡፡ *በሴይር ኰረብታማ አገር፤* ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ ያለው ተራራማ ስፍራ ነው፡፡

2፥5 *ከየትኛውም ምድራቸው ... መሬት ስለማልሰጣችሁ፤* ቍ 9:19 ይመ፡፡ እስራኤላውያን ከዔዶም፣ ከሞዓብና ከአሞናውያን ሕዝቦች ጋር የሥጋ ዝምድና ስለ ነበራቸው፣ እነዚህን ሕዝቦች ምንም ሳይነኩ እንዲያልፉ እግዚአብሔር ለሙሴ ነገረው፡፡ እስራኤላውያን መውረስ ያለባቸው ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተ ምሥራቅ የሚገኙትንና በአሞራውያን የተያዙትን ስፍራዎች ብቻ ነው (ቍ24፤ 3፥2 ይመ)፡፡ *ሰጥቼዋለሁ፤* ቍ 9:19 ይመ፡፡ እግዚአብሔር ከዮርዳኖስ ወንዝ ባሻገር የሚገኘውን ምድርና የከነዓናውያንን ምድር ለእስራኤላውያን እንደ ሰጣቸው ሁሉ፣ ለዔሳው ዝርያዎችና (ለዔዶማውያን) ለሎጥ ዝርያዎች (ለሞዓባውያንና ለአሞናውያን) ምድራቸውን ሰጥቶአቸዋል፡፡

2፥8 *ኤላትና ዔጽዮንጋብር፤* ከአካባ ባሕረ ሰላጤ በላይኛው ጫፍ በኩል የሚገኙ ስፍራዎች ናቸው፤ "የዓረባ መንገድ" የተባለውም ከዚሁ ባሕረ ሰላጤ ሰሜናዊ ጫፍ ተነሥቶ እስከ ምሥራቃዊው የሞዓብ ምድር ድረስ ይደርሳል፡፡

2፥9 *ዔር፤* ይህ ስፍራ የት እንደሚገኝ አይታወቅም፡፡

2፥10 *ዔናቃውያን፤* የ1፥28 ማብ ይመ፡፡ *ኤሚማውያን፤* ምናልባት "ሽብር" ማለት ሊሆን ይችላል፡፡

2፥11 *ራፋይማውያን፤* ግዙፍና ረጃጅም የሆኑ የጥንት ሰዎች ናቸው፡፡

2፥12 *ሖራውያን፤* የዘፍ 14፥6 ማብ ይመ፡፡ *እግዚአብሔር ... በሰጠው ምድር፤* ይህ ምድር (1) ከዮርዳኖስ ባሻገር የሚገኙ ቦታዎችን (2፥24-3፥20 ይመ)፣ (2) ራሱን የከነዓንን ምድር ወይም (3) ከዮርዳኖስ ማዶ የሚገኘውን ስፍራና የከነዓንን ምድር በአንድነት ሊሆን ይችላል፡፡

2፥13 *ዘሬድ፤* ከምሥራቅ አካባቢ ተነሥቶ ወደ ደቡባዊው የሙት ባሕር መጨረሻ ክፍል የሚፈስ ትልቅ ጅረት ነው፡፡

2፥14 *ሠላሳ ስምንት ዓመት፤* የ1፥3 ማብ ይመ፡፡

ድረስ የእግዚአብሔር (ያህዌ) እጅ በእነርሱ ላይ ነበር።

[16]በሕዝቡ መካከል የነበሩት የመጨረሻዎቹ ተዋጊዎች ከሞቱ በኋላ፣ [17]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲህ አለኝ፤ [18]"የሞዓብ ዳርቻ ዔርን ዛሬውኑ ታልፋላችሁ። [19]ከየትኛውም የአሞናውያን ምድር ለእናንተ ርስት ስለማልሰጣችሁ፣ አሞናውያን ዘንድ በደረሳችሁ ጊዜ አታስቸግሯቸው፤ ለጦርነትም አታነሣሡአቸው። ያን ቦታ ርስት አድርጌ ለሎጥ ዘሮች ሰጥቻቸዋለሁ።"

[20]ያም ደግሞ በዚያ ይኖሩ የነበሩት የረፋይማውያን ምድር እንደ ሆነ ይቈጠር ነበር፤ አሞናውያን ግን ዘምዙማውያን ብለው ይጠሯቸው ነበር። [21]ዘምዙማውያን ብርቱዎች፣ ቍጥራቸው የበዛና እንደ ዔናቃውያን ቁመተ ረጃጅሞች ነበሩ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) ከእነርሱ ፊት አጠፋቸው፤ እነርሱም አሳደዷቸው በምትካቸውም ሰፈሩበት። [22]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሖሪውያንን ከፊታቸው ባጠፋ ጊዜ፣ በሴይር ለሚኖሩት የዔሳው ዘሮች ያደረገው ይህንኑ ነበር። እነርሱም አሳደው በማስወጣት ባስለቀቁት ስፍራ ላይ እስከ ዛሬ ይኖራሉ። [23]እስከ ጋዛ ድረስ ባሉት መንደሮች የኖሩትን ኤዋውያን በተመለከተም፣ ከከፍቶር* ወጥተው የመጡት ከፍቶራውያን እነርሱን አጥፍተው መኖሪያቸውን እዚያው አደረጉ።

## የሐሴቦን ንጉሥ የሴዎን ድል መነሣት

[24]"አሁኑኑ ተነሡና የአርኖንን ወንዝ ተሻገሩ፤ እነሆ፣ የሐሴቦንን ንጉሥ፣ አሞራዊውን ሴዎንንና አገሩን በእጃችሁ ሰጥቻችኋለሁ፤ ምድሩን መውረስ ጀምሩ፤ ጦርነት ግጠሙት። [25]ከሰማይ በታች ባሉ አሕዛብ ሁሉ ላይ፣ ማስደንገጣችሁና ማስፈራታችሁ እንዲያድርባቸው ከዚህች ከዛሬዋ ዕለት እጀምራለሁ። ስለ እናንተ ሰምተው ይረበተበታሉ፤ ከእናንተ የተነሣም ይጨነቃሉ።"

[26]ከቅዴሞት ምድረ በዳም ለሐሴቦን ንጉሥ ለሴዎን የሰላም ቃል እንዲያደርሱለት እንዲህ በማለት መልእክተኞች ላክሁ፤ [27]"በአገርህ አቋርጠን እንድናልፍ ፍቀድልን፤ ከዋናው መንገድ አንወጣም፤ ቀኝም ግራም አንልም። [28]የምንበላውን ምግብ፣ የምንጠጣውንም ውሃ፣ በጥሬ ብር ሽጥልን። በእግር እንድናልፍ ብቻ ፍቀድልን፤ [29]በሴይር የሚኖሩ የዔሳው ዘሮችና በዔር የሚኖሩ ሞዓባውያን እንዳደረጉልን ሁሉ፣ እንተም አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጠን ምድር ለመግባት ዮርዳኖስን እስክንሻገር ድረስ እንደዚሁ አድርግልን።" [30]ይሁን እንጂ የሐሴቦን ንጉሥ ሴዎን እንድናልፍ አልፈቀደልንም። ምክንያቱም አምላካችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አሁን እንዳደረገው ሁሉ እርሱን በእጃችሁ አሳልፎ ለመስጠት መንፈሱን አደንድኖት፣ ልቡንም አጽንቶት ነበር።

[31]እግዚአብሔርም (ያህዌ)፣ "እነሆ፣ ሴዎንንና አገሩን ለእናንተ አሳልፌ ልሰጣችሁ ተነሥቻለሁ፤ አሁንም እርሱን አሸንፋችሁ ምድሩን ለመውረስ ተነሡ" አለኝ።

[32]ሴዎንና መላው ሰራዊቱ በያህጽ ጦርነት ሊገጥሙን በወጡ ጊዜ፣ [33]አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጃችን ላይ ጣለው፤ እኛም፣ እርሱን ከወንድ ልጆቹና ከመላው ሰራዊቱ ጋር አንድ ላይ መታነው። [34]በዚያን ጊዜ ከተሞቹን በሙሉ ወስደን የሚኖሩባቸውን ወንዶች፣ ሴቶችና ልጆቻቸውን ጭምር ፈጽመን አጠፋናቸው**፤ አንዳቸውንም በሕይወት አላስቀረንም። [35]ከብቶቻቸውንና ከየከተሞቻቸው ያገኘነውን ምርኮ ግን ለራሳችን አደረግን። [36]በአርኖን ሸለቆ ጫፍ ካለችው ከአሮዔርና በሸለቆው ውስጥ ከምትገኘዋ ከተማ አንሥቶ እስከ ገለዓድ ካሉት ከተሞች አንዳቸውም እንኳ ሊገቱን አልቻሉም። አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ሁሉንም አሳልፎ ሰጠን። [37]ይሁን እንጂ አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሰጠው ትእዛዝ መሠረት፣ ወደ ማናቸውም የአሞናውያን ምድር ወይም በያቦቅ ወንዝ መውረጃ ወዳለው ምድር፣ ወይም ደግሞ በኰረብቶች ወዳሉት ከተሞች ዙሪያ ዐልፋችሁ አልሄዳችሁም።

## የባሳን ንጉሥ የዐግ መሸነፍ

3 ከዚያም፣ ተመልሰን የባሳንን መንገድ ይዘን ወጣን፤ የባሳን ንጉሥ ዐግም ከመላው ሰራዊቱ ጋር ሆኖ በኤድራይ ጦርነት ሊገጥመን ተነሣ። [2]እግዚአብሔር (ያህዌ)፣ "እርሱን፣ መላው ሰራዊቱንና ምድሩን በእጅህ አሳልፌ ስለ

2፥18 ዘኍ21፥15
2፥19 ቍ9፤ ዘፍ19፥38፤2ዜና20፥10
2፥20 ዘፍ14፥5
2፥21 ቍ10
2፥22 ዘፍ14፥6
2፥23 ዘፍ10፥14፡ 19፤ኢያ13፥3፤ 18፥23፤2ነገ17፥31፤ ኤር47፥4፤አሞ9፥7
2፥24 ዘኍ21፥13-14፤ ዘዳ1፥7፤3፥6፤ መሳ11፥13፡18
2፥25 ዘፍ35፥5፤ ዘፀ15፥14-16፤ ዘዳ11፥25፤ኢያ2፥9፡ 11፤1ዜና14፥17፤ 2ዜና14፥14፤17፥10፤ 20፥29፤ኢሳ2፥19፤ 13፥13፤19፥16፤
2፥26 ዘዳ1፥4፤ 20፥10፤ኢያ13፥18፤ መሳ11፥21-22፤ 21፥13፤2ሳሙ20፥19፤ 1ዜና6፥79
2፥27 ዘኍ21፥21-22
2፥28 ዘዳ23፥4፤ ዘኍ20፥19
2፥30 ዘፀ4፥21፤ 14፥7፤መሳ14፥4፤ 1ነገ12፥15፤ሰቆ3፥65፤ ሮሜ9፥18
2፥31 ዘፍ12፥7
2፥32 ዘኍ21፥23
2፥33 ዘፀ23፥31፤ ዘኍ21፥24፤ዘዳ7፥2፤ 31፥5
2፥35 ዘፍ34፥29፤ 49፥27፤ዘዳ3፥7
2፥36 ዘኍ32፥34፡ 39፤መዝ44፥3
2፥37 ቍ18-19፤ ዘፍ32፥22፤ዘኍ21፥24
3፥1 ዘኍ32፥19፡ 21፥33
3፥2 ኢያ10፥8፤2ነገ 19፥6፤ኢሳ7፥4

*23 ቀርጤስ ነች
**34 የዕብራይስጡ ቃል አንድን ነገር ወይም አንድን ሰው ሙሉ በሙሉ በማጥፋት ለእግዚአብሔር መስጠትን የሚያሳይ ነው።

2፥20 *ዘምዙማውያን፤* ምናልባት፣ "አጕረምራሚዎች" ማለት ሊሆን ይችላል፤ በዘፍ 14፥5 ላይ ከተጠቀሱት ከ"ዙዚምናውያን" ጋርም አንድ ሊሆኑ ይችላሉ።

2፥23 *ኤዋውያን፤* ከፍልስጥኤማውያን በፊት ይኖሩ የነበሩ ሕዝቦች ሊሆኑ ይችላሉ፤ ይህ ካልሆነ ግን ስለ ማንነታቸው ምንም የሚታወቅ ነገር የለም ማለት ነው (ኢያ 13፥3)። *ከፍቶራውያን፤* የዘፍ 10፥14 ማብ ይመ።

2፥24 *አርኖን፤* የዘኍ 21፥10-13 ማብ ይመ።

2፥26 *ቅዴሞት፤* "ምሥራቃዊ ክልሎች" ማለት ነው።

2፥30 *መንፈሱን አደንድኖት፣ ልቡንም አጽንቶት፤* በብሉይ ኪዳን ድርጊቶች፣ አብዛኛውን ጊዜ የሚያያዙት ከድርጊቱ መንሥኤ ወይም ከአካባቢያዊ ሁኔታዎች ወይም ድርጊቱን ከፈጸሙት ሰዎች ጋር ሳይሆን ከእግዚአብሔር ጋር ነው። ሴዎን እስራኤላውያን እንዳያልፉ ሆን ብሎ መንገድ ዘጋባቸው፤ ነገር ግን የሴዎንን ምድር ለእስራኤል የሚሰጥ እግዚአብሔር ነው (የዘፀ 4፥21 ማብ ይመ)።

2፥32 *ያህጽ፤* የኢሳ 15፥4 ማብ ይመ።

2፥34 *ፈጽመን አጠፋናቸው፤* ይህ ሐረግ የተገለጸበት የዕብራይስጡ ቃል መጥፋት ያለበትን ማንኛውንም ሰውና ነገር ያመለክታል። መጥፋት የማይችሉ እንደ ወርቅ፣ ብርና ናስ ያሉ ነገሮች ግን የእግዚአብሔር ንብረት ተብለው በጥንቃቄ ይቀመጡ ነበር። ሰዎችንና ነገሮችን ጨርሶ ማጥፋት ወርቅ፣ ብርና ናስ በድል አድራጊዎች ዘንድ ዋጋ የሌላቸው አርጓቸዋል፤ ይሁን እንጂ እንደ እግዚአብሔር ንብረት ተቈጥረው ለእግዚአብሔር ይሰጡ ነበር። ስለዚህ ቃሉ አንዳንድ ጊዜ፣ "አጠፉ" ተብሎ ሌላ ጊዜ ደግሞ፣ "አስረከቡ" ተብሎ (ለምሳሌ ኢያ 6፥17 ይመ) ተተርጕሞአል። እግዚአብሔር የእርሱ የጦር ወታደር ሆኖ ያገለገለው ሕዝብ የከብቱንና የንብረቱን ምርኮ ለራሳቸው እንዲወስዱ በሚያደርግበት ጊዜ ይህ ድርጊት በከፊል ይሻራል (ቍ35፤ 3፥7፤ ኢያ 8፥2 ይመ)።

2፥36 *አሮዔር፤* የኢሳ 17፥2 ማብ ይመ። *ገለዓድ፤* የዘፍ 31፥21 ማብ ይመ።

2፥37 *ያቦቅ፤* የዘፍ 32፥22 ማብ ይመ።

ስጠሁህ፣ አትፍራው፤ ሐሴቦንን ይዞ በነበረው በአሞራውያን ንጉሥ በሴዎን ላይ ያደረግህ በትን በእርሱም ላይ አድርግበት” አለኝ::

[3]ስለዚህ *አምላካችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የባሳንን ንጉሥ ዐግንና ሰራዊቱን ሁሉ እንደዚሁ በእጃችን ላይ ጣላቸው፤ እኛም አንድ እንኳ በሕይወት ሳናስቀር አጠፋናቸው:: [4]በዚያን ጊዜ ከተሞቹን ሁሉ ያዝን፤ የዐግ ግዛት ከሆነው፣ በባሳን ከሚገኘው ከጠቅላላው የአ ርጎብ ክልል ሥልሳ ከተሞች ውስጥ፣ እኛ ያልያዝነው አንድም ከተማ አልነበረም:: [5]እነዚህ ከተሞች ሁሉ ከፍ ባሉ ቅጥሮች፣ በመዝጊያዎችና በመወርወሪያዎች የተመሸጉ ነበሩ፤ እንዲሁም ቅጥር የሌላቸው አያሌ መንደሮች ነበሩ:: [6]በእያንዳንዱ ከተማ ያሉትን ወንዶቹን፣ ሴቶቹንና ልጆቻቸውን ጭምር በማ ጥፋት፣ በሐሴቦን ንጉሥ በሴዎን ላይ እንዳ ደረግነው ሁሉ፣ እነዚህንም ፈጽመን ደመሰ ስናቸው[ሠ]:: [7]ከብቱን በሙሉና ከየከተሞቻቸው የማረክነውን ሁሉ ግን ለራሳችን አደረግን::

[8]ስለዚህ በዚያን ጊዜ ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ የሚገኘውን፣ ከአርኖን ሸለቆ እስከ አርሞንዔም ተራራ ያለውን ግዛት፣ ከእነዚህ ከሁለቱ የአሞራውያን ነገሥታት ላይ ወሰድን ባቸው:: [9]አርሞንዔምን፣ ሲዶናውያን ሢርዮን ብለው ሲጠሩት፣ አሞራውያን ግን ሳኔር ይሉታል:: [10]በከፍታው ቦታ ላይ የሚገኙትን ከተሞች በሙሉ፣ ገለዓድን እንዳለ፣ እስከ ሰልካና እስከ ኤድራይ ያለውን ባሳንን ሁሉ እንዲሁም በባሳን ውስጥ የሚገኙትን የዐግ ግዛት ከተሞች በእጃችን አደረግን:: [11]ከራ ፋይማውያን ወገን የተረፈ የባሳን ንጉሥ ዐግ ብቻ ነበር:: ዐልጋው[ረ] ከብረት የተሠራ ቁመ ቱም ዘጠኝ ክንድ፣ ስፋቱ ደግሞ አራት ክንድ[ሰ] ነበር:: ይህም እስካሁን በአሞናውያን ከተማ በረባት ይገኛል::

## እስራኤላውያን ምድሪቱን መከፋፈላቸው

[12]በዚያን ጊዜ ከያዝነው ምድር ላይ በአር ኖን ሸለቆ አጠገብ ካለችው ከአሮዔር አንሥቶ በስተ ሰሜን ያለውን ግዛት፣ በተጨማሪም ኰረብታማውን የገለዓድ አገር እኩሌታ ከነ ከተሞቹ ለሮቤላውያንና ለጋዳውያን ሰጠ ኋቸው:: [13]ቀሪውን የገለዓድ ምድርና የዐግ ግዛት የሆነውን ባሳንን በሙሉ ለምናሴ ነገድ እኩሌታ ሰጠሁ:: በባሳን የሚገኘው መላው የአርጎብ ክልል የራፋይማውያን ምድር በመባል ይታወቅ ነበር:: [14]ከምናሴ ነገድ የሆነው ኢያዕር፣ እስከ ጌሹራውያንና እስከ ማዕካታ ውያን ወሰን ድረስ የሚገኘውን መላውን የአርጎብ ምድር ወሰደ፤ ምድሪቱም በስሙ ተጠራች[ሸ]፤ ከዚሁ የተነሣ ባሳን እስከ ዛሬ ድረስ ሐቦት ኢያዕር ትባላለች:: [15]ገለዓድንም ለማኪር ሰጠሁት:: [16]ነገር ግን የሸለቆውን እኩሌታ ወሰን በማድረግ ከገለዓድ አንሥቶ እስከ አርኖን ሸለቆ፣ ከዚያም የአሞናውያን ድንበር እስከ ሆነው እስከ ያቦቅ ወንዝ ያለ ውን ግዛት ለሮቤላውያንና ለጋዳውያን ሰጠ ኋቸው:: [17]የምዕራቡ ወሰን፣ በዓረባ የሚ ገኘው ዮርዳኖስ ሲሆን፣ ይኸውም ከፈስጋ ተረተሮች በታች፣ ከኪኔሬት አንሥቶ የጨው ባሕር[ቀ] እስከሚባለው እስከ ዓረባ ባሕር ድረስ ነው::

[18]በዚያን ጊዜ እኔ እንዲህ ብዬ አዘዝኋችሁ፤ “*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ይህችን ምድር ርስት አድርጎ ለእናንተ ሰጥቶአችኋል፤ ይሁን እንጂ የአካል ብቃት ያላቸው ሰዎቻችሁ ሁሉ ለጦርነት ዝግጁ ሆነው ከወንድሞቻችሁ ከእስራኤላውያን ፊት በመቅደም መሻገር አለባቸው:: [19]ሆኖም ሚስቶቻችሁና ልጆቻችሁ፣ (ብዙ ከብቶች እንዳሏችሁም ስለማውቅ) ከብቶቻችሁም በሰጠኋችሁ ከተሞች ውስጥ ይቈዩ፤ [20]ይኸውም፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለእናንተ እንዳደረገው ሁሉ ወንድሞቻችሁን እስኪያሳር ፋቸውና *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከዮርዳኖስ ማዶ የሚሰጣቸውን ምድር እነርሱም እንደዚሁ እስኪወርሱ ድረስ ነው፤ ከዚያ በኋላ እያንዳንዳችሁ ወደ ሰጠኋችሁ ርስት ትመለ ሳላችሁ::”

3፥3 ዘኍ21፥24:35
3፥4 ቍ13፤ ዘኍ21፥24:33
3፥6 ዘዳ2፥24
3፥7 ዘዳ2፥35
3፥8 ዘኍ32፥33፤ ዘዳ4፥48፤ ኢሱ11፥3:17፤12፥1፤ 13፥5:8-12፤መሳ3፥3፤ 1ዜና5፥23፤መዝ42፥6፤ 89፥12፤133፥3፤ መሓ4፥8
3፥9 1ዜና5፥23፤ መዝ29፥6፤መሓ4፥8፤ ሕዝ27፥5
3፥10 ኢሱ12፥5፤ 1ዜና5፥11
3፥11 ዘፍ14፥5፤ ኢሱ13፥25፤15፥60፤ 2ሳሙ11፥1፤12፥26፤ 17፥27፤1ዜና20፥1፤ ኤር49፥2፤ሕዝ21፥20፤ 25፥5፤አሞ1፥14
3፥12 ዘዳ2፥36
2፥13 ዘፍ14፥5፤ ዘዳ29፥8
3፥14 ዘኍ32፥41፤ ኢሱ12፥5፤13፥11፡ 13፤ 19፥47፤2ሳሙ10፥6፤ 23፥34፤2ነገ25፥23፤ 1ዜና4፥19፤ መዝ49፥11፤ኤር40፥8
3፥15 ዘፍ50፥23፤ ዘኍ32፥39-40
3፥16 ዘኍ21፥24
3፥17 ዘፍ14፥3፤ ዘኍ34፥11፤ዘዳ1፥1፤ ሳሙ2፥29፤4፥7፤ ሕዝ 47፥8
3፥18 ዘኍ32፥17፤ ኢሱ1፥13
3፥19 ዘኍ32፥16፤ ኢሱ1፥14

[ሠ]6 የ2፥34 አማራጭ ትርጒም ይመ::
[ረ]11 ወይም፣ *ድንጋይ ተጠርቦ የተዘጋጀ የሬሳ ሣጥን*
[ሰ]11 ቁመቱ 4 ሜትር ስፋቱ 1.8 ሜትር ያህል ነው::
[ሸ]14 ወይም፣ *የኢያዕር መኖሪያ ተብላ ተጠራች*
[ቀ]17 ይኸውም የሙት ባሕር ነው::

3፥3 *ዐግን ... በእጃችን ላይ ጣላቸው፤* በ2፥26-37 ላይ ሌሎችን አሳልፎ እንደሰጣቸው ማለት ነው::

3፥4 *የአርጎብ ክልል፤* ከዚህ ክፍል በስተቀር በሌላ ስፍራ በባሳን ምድር ውስጥ እንደሚገኝ አልተጠቀሰም (ቍ 13-14፤ 1ነገ 4፥13 ይመ):: *ሥልሳ ከተሞች፤* ከተሞቹ ትልቅና ዙሪያቸውም የተቀጠረ ነበር (1ነገ 4፥13)፤ ይህም የሚያሳየው በከተሞቹ ውስጥ ከፍተኛ የሕዝብ ቍጥር እንደ ነበረ ነው (ቍ 5 ይመ)::

*3፥6-7፤* የ2፥34 ማብ ይመ::

3፥8 *አርሞንዔም ተራራ፤* ከዓመት እስከ ዓመት ጫፉ በበረዶ የተሸፈነ ሲሆን፣ ከፍታው እስከ 9200 ጫማ የሚደርስና በሊባኖስ አገር ከሚገኙ ታላላቅና ውብ ተራሮች ውስጥ አንዱ ነው::

3፥9 *ሢርዮን፤* ለአርሞንዔም ተራራ የተሰጠው ይህ ስም ሙሴ በነበረበት ዘመን በአንድ የከነዓናውያን ጽሑፍ ውስጥ ተገኝቶአል:: *ሳኔር፤* ለአርሞንዔም ተራራ የተሰጠው ይህ ስም በአሦራውያንም ጽሑፍ ይገኛል::

3፥10 *ሰልካ፤* የባሳንን ምሥራቃዊ ድንበር የሚያመለክት ከተማ ነው (ኢሱ 13፥11 ይመ)::

3፥11 *ዐልጋውም ከብረት የተሠራ፤* በባሳን ምድር፣ ከባልጩት ድንጋይ የተሠራ በድን የሚያርፍበት ዐልጋ ሲሆን፣ “ዐልጋ” እን ዲሁም “ብረት” የሚሉትን ቃላት ለመግለጽ የገቡት የዕብራይስጥ ቃላት በአንድነት ሲጣመሩ ይህን ያንጸባርቃሉ:: ዐልጋው እውነተኛ ዐልጋ ከሆነ የሚሠራው ከእንጨት ስለ ሆነ ምናልባት ይህ የሚያመ ለክተው የዐልጋው መጋጠሚያዎች ከብረት መሠራታቸውን ነው፤ ለምሳሌ “የብረት ሠረገላዎች” እንደሚባለው ዐይነት ማለት ነው (የኢሱ 17፥16 ማብ ይመ):: *በአሞናውያን ከተማ በረባት፤* አዲስ ኪዳን በተጻፈበት ዘመን ፊላደልፍያ ተብላ የምትጠራ ሲሆን፣ ረባት የጥንቷ የአሞናውያን ዋና ከተማ ነበረች (አሞ 1፥13-14):: በአሁኑ ጊዜ ስሟ አማን ሲሆን፣ የዮርዳኖስ መንግሥት ዋና ከተማ ናት።

3፥12-20፤ ዘኍ 32፤34፥13-15 ይመ::

3፥14 *ኢያዕር ... ሐቦት ኢያዕር፤* “የኢያዕር ሰፈር” ወይም “የኢ ያዕር መንደር” ማለት ነው፤ እንዲሁም የመሳ 10፥3 ማብ ይመ:: *ጌሹራ ውያንና ... ማዕካታውያን፤* ከሌሎቹ ጋር ሲነጻጸሩ አነስተኛ መንግሥታት ናቸው፤ ጌሹር ከገሊላ ባሕር በስተ ምሥራቅ ሲገኝ፣ ማዕ ካት ደግሞ ከሜሮን ውሃ በስተ ሰሜን ይገኛል (የኢሱ 11፥5 ማብ ይመ)::

3፥15 *ማኪር፤* የዘፍ 50፥23 ማብ ይመ::

3፥17 *ኪኔሬት፤* የማር 1፥16 ማብ ይመ:: *ፈስጋ፤* በስተ ምሥራቅ በዐምባው ጫፍ ላይ የሚገኝና የሙት ባሕርን ወደታች የሚያይ ቦታ ነው::

3፥20 *እስኪያሳርፋቸው፤* ፍጹም ዕረፍትንና መረጋጋትን የሚያሳይ

## ሙሴ ዮርዳኖስን እንዳይሻገር መከልከሉ

[21]በዚያን ጊዜ ኢያሱን እንዲህ ስል አዘዝሁት፤ "አምላካችሁ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በእነዚህ በሁለቱ ነገሥታት ላይ ያደረገውን ሁሉ በገዛ ዓይንህ አይተሃል፤ አሁንም ዐልፈህ በምትሄድባቸው መንግሥታት ላይ ሁሉ እግዚአብሔር ይህንኑ ይደግመዋል። [22]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) *ራሱ* ይዋጋላችኋልና አትፍሯቸው።"

[23]በዚያን ጊዜ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዲህ ብዬ ለመንሁት፤ [24]"ጌታ *እግዚአብሔር* (አዶናይ ያህዌ) ሆይ፤ ታላቅነትህንና ብርቱ ክንድህን ለእኔ ለባሪያህ እነሆ፤ ማሳየት ጀምረሃል፤ ለመሆኑ በሰማይም ሆነ በምድር፣ አንተ የምታደርጋቸውን ሥራዎችና ታላላቅ ድርጊቶች መፈጸም የሚችል አምላክ ማነው? [25]አሁንም ከዮርዳኖስ ማዶ ያለችውን ያችን መልካሚቱን ምድር፣ ውብ የሆነችውን ኰረብታማ አገርና ሊባኖስን እንዳይ ፍቀድልኝ።"

[26]እግዚአብሔር ግን በእናንተ ሰበብ ተቈጥቶኝ ነበርና አልሰማኝም፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዲህ አለኝ፤ "ይበቃል፤ ከእንግዲህ ወዲያ ስለዚህ ነገር አታንሣብኝ። [27]ወደ ፈስጋ ተራራ ጫፍ ውጣ፤ ወደ ምዕራብና ወደ ሰሜን፣ ወደ ደቡብና ወደ ምሥራቅም ተመልከት። አንተ ዮርዳኖስን ስለማትሻገር፣ ምድሪቱን በዐይንህ ብቻ እያት። [28]ነገር ግን ሕዝቡን መርቶ በማሻገር የምታያትን ምድር እንዲወርሱ የሚያደርጋቸው ስለ ሆነ፣ ኢያሱን ላከው፤ አደፋፍረው፤ አበረታታውም።" [29]ስለዚህ እኛ በቤተ ፌጎር አጠገብ ባለው ሸለቆ ውስጥ ቈየን።

## ሙሴ እስራኤላውያን እንዲታዘዙ ማስጠንቀቁ

**4** አሁንም እስራኤል ሆይ፤ በሕይወት እንድትኖሩ፣ የአባቶቻችሁ *አምላክ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጣችሁ ምድር እንድትገቡና እንድትወርሱ የማስተምራችሁን ሥርዐትና ሕግ ስሙ፤ ጠብቋቸውም። [2]ባዘዝኋችሁ ላይ አትጨምሩ፤ ከእርሱም አትቀንሱ፤ ነገር ግን የምሰጣችሁን የአምላካችሁን *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ትእዛዞች ጠብቁ።

[3]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በብዔልፌጎር ላይ ምን እንዳደረገ በዐይናችሁ አይታችኋል፤ አምላካችሁ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከመካከላችሁ ብዔልፌጎርን የተከተሉትን ሁሉ አጥፍቶአቸዋል፤ [4]አምላካችሁን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) የተከተላችሁት እናንተ ሁላችሁ ግን ይኸው እስከ ዛሬ በሕይወት አላችሁ።

[5]ገብታችሁ በምትወርሷት ምድር፣ እንድትፈጽሟቸው እግዚአብሔር *አምላኬ* (ኤሎሂም ያህዌ) ባዘዘኝ መሠረት ሥርዐትንና ሕግን አስተምሬአችኋለሁ። [6]በጥንቃቄ ጠብቋቸው፤ ስለ እነዚህ ሥርዐቶች ሁሉ ለሚሰሙና፣ "በእውነቱ ይህ *ታላቅ* ሕዝብ የቱን ያህል ጥበበኛና አስተዋይ ነው" ለሚሉ ሕዝቦች ይህ ጥበባችሁንና ማስተዋላችሁን ይገልጣልና። [7]በምንጠራው ጊዜ ሁሉ *አምላካችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለእኛ ቅርብ እንደ ሆነ አማልክቱ የሚቀርቡት ሌላ *ታላቅ* ሕዝብ ማነው? [8]ዛሬ እኔ በፊታችሁ እንዳስቀመጥሁት ሕግ ያለ፣ ጽድቅ የሆነ ሥርዐትና ሕግ ያሉት ሌላ *ታላቅ* ሕዝብስ ማነው?

[9]ዐይኖቻችሁ ያዩዋቸውን ነገሮች እንዳትረሱ፣ ደግሞም በሕይወት እስካላችሁ ድረስ ከልባችሁ እንዳይጠፉ ብቻ ተጠንቀቁ፣ ነቅታችሁም ራሳችሁን ጠብቁ። እነዚህን ለልጆቻችሁና ከእነርሱ በኋላ ለሚወለዱት ልጆቻቸው አስተምሯቸው። [10]"በምድሪቱ በሚኖሩበት ጊዜ ሁሉ እኔን ማክበር እንዲማሩ፣ ለልጆቻቸውም እንዲያስተምሩ ቃሌን ይሰሙ ዘንድ ሕዝቡን በፊቴ ሰብስብ" ባለኝ ጊዜ፣ በኮሬብ *በአምላካችሁ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት

3፥22 ዘፀ14፥14፤ ዘዳ1፥29፤7፥18፤ 20፥1፤31፥6፤2ዜና32፥8፤መዝ23፥4፤ ኢሳ41፥10
3፥23 ዘዳ1፥37፤ 31፥2፤32፥52፤34፥4
3፥24 ዘፀ8፥10፤ ዘዳ5፥24፤11፥2፤32፥3፤ 8፥10፤2ሳሙ7፥22፤ መዝ71፥16፤106፥2፤ 145፥12፤150፥2
3፥25 ዘዳ1፥7፤ 4፥22፤ኢሱ1፥4፤9፥1፤ 11፥17፤12፥7፤13፥5፤ መሳ3፥3፤9፥15፤ 1ነገ4፥33
3፥26 ቍ27፤ ዘዳ1፥37፤31፥2
3፥27 ቍ26፤ ዘፍ13፥14፤ዘኍ20፥12፤21፥20፤27፥12፤ ዘዳ32፥52
3፥28 ዘኍ27፥18-23፤ ዘዳ31፥7፤ዘዳ1፥38፤ 31፥3፡23
3፥29 ዘኍ23፥28፤ ዘዳ4፥46፤34፥6፤ ኢሱ13፥20
4፥1 ዘሌ18፥4፡5፤ ዘዳ1፥3፤30፥15-20፤ ሮሜ10፥5
4፥2 ዘሌ22፥31፤ ዘዳ10፥12-13፤ 12፥32፤ኢሱ1፥7፤ ምሳ30፥6፤ኤር26፥2፤ መክ12፥13፤ ራእ22፥18-19
4፥3 ዘኍ25፥1-9፤ መዝ106፥28
4፥5 ዘፀ18፥20፤ ዘሌ27፥34፤መዝ71፥17፤ 119፥102፤ኤር32፥33፤ ዕዝ9፥11
4፥6 ዘዳ29፥9፤ 30፥19-20፤32፥46-47፤ 1ነገ2፥3፤መዝ19፥7፤ 119፥98፤ምሳ1፥7፤ ኢዮ1፥1፤28፥28፤ መዝ111፥10፤ ምሳ2፥5፤3፥7፤9፥10፤ መክ12፥13፤ ሕዝ 5፥5፤2ጢሞ3፥15
4፥7 ቍ32-34፤ ዘኍ23፥21፤2ሳሙ7፥23፤መዝ46፥1፤ሐሥ17፥27
4፥8 መዝ89፥14፤ 97፥2፤119፥7፡62፡144፡160፡172፤ሮሜ3፥2
4፥9 ዘፍ14፥14፤18፥19፤ዘፀ10፥2፤23፥13፤ዘዳ6፥20-25፤ኤፌ6፥4
4፥10 ቍ9፤ዘፀ3፥1፤ 20፥20፤12፥1፤ዘዳ12፥1፤14፥23፤ 17፥19፤31፥12-13፤ መዝ2፥11፤111፥10፤147፥11፤ኢሳ8፥13፤ ኤር32፥40

---

ነው፤ ይህም ዕረፍት ከውጭ ከሚመጣ ዛቻና ጭቆና ነጻ መሆንን እንዲሁም ከውስጥ በሚፈጠር የእርስ በርስን ግጭት፣ ረሃብን ወይም ቸነፈርን ያመለክታል (12፥9-10፤ 25፥19 ይመ፤ እንዲሁም የኢሱ 1፥13፤ የ1ነገ 5፥4፤ የዕብ 4፥1-11 ማብ ይመ)።

3፥22 *እግዚአብሔር አምላካችሁ ራሱ፤* እስራኤል ያደረገቻቸው ፍልሚያዎች ሁሉ የሚያረጋግጡት ያለ እግዚአብሔር ርዳታ እስራኤል ድል ልታገኝ የማትችል መሆኗን ነው። ድል የሚያስገኘው የእስራኤል ኀይል ሳይሆን የእግዚአብሔር ኀይል ነው። ሙሴ የእስራኤልን ወኔና እምነት በዚህ እውነት አነሣሣ (1፥30፤ 2፥21-22፡31፤20፥4 ይመ)።

*3፥23-25፤* ሙሴ ወደ ተስፋዪቱ ምድር ለመግባት ያቀረበው የመጨረሻ ልመና ነው (1፥37 እና ማብ 31፥2 ይመ)።

3፥26 *በእናንተ ሰበብ፤* የ1፥37 ማብ ይመ።

3፥27 *ወደ ፈስጋ ተራራ ጫፍ ውጣ፤* ሙሴ ይህን ያደረገው እስራኤላውያን በተስፋዪቱ ምድር እንዴት መኖር እንዳለባቸው የሕጉን መጽሐፍ እያብራራ ካዘጋጃቸው በኋላ ነበር (32፥48-52፤ 34፥1-6 ይመ)። *ፈስጋ፤* የቍ 17 ማብ ይመ። *ወደ ምዕራብና ወደ ሰሜን፣ ወደ ደቡብና ወደ ምሥራቅም ተመልከት፤* እንደ አብርሃም (ዘፍ 13፥14 ይመ)፣ ሙሴም የተስፋዪቱን ምድር የሚወርሰው በዘርያዎቹ አማካይነት ብቻ ነው (34፥1-4 ይመ)።

3፥28 *ኢያሱን ላከው፤* 31፥7-8 ይመ።

3፥29 *ቤተ ፌጎር፤* የፌጎር ቤት ማለት ሲሆን፣ ምናልባት "የፌጎር በኣል" የተባለ ጣዖት የሚመለክበትን ስፍራ ሳያመለክት አይቀርም (ዘኍ 23፥28፤ 25፥3፡5)።

4፥1 *እስራኤል ሆይ፤ ... ስሙ፤* ሕዝቡ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ እንዲሰማና እንዲታዘዝ የቀረበው ጥሪ በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ተደጋግሞ የሚወጣ መሪ ሐሳብ ነው (ለምሳሌ 5፥1 6፥3-4፤ 9፥1፤ 20፥3 ይመ)፤ በሌሎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትም ተመሳሳይ ጥሪ ይገኛል። በተጨማሪም የ6፥4-9 ማብ ይመ።

4፥2 *አትጨምሩ፤ አትቀንሱ፤* እግዚአብሔር የሚሰጠው መገለጥ በቂ ነው። መገለጡን በሙሉ ልብ መታዘዝ እንጂ ከእርሱ አንዳች ማጉደል ወይም መጨመር ከቶ አይፈቀድም (12፥32፤ ምሳ 30፥6፤ ገላ 3፥15፤ ራእ 22፥18-19 ይመ)።

4፥4 *የተከተላችሁት፤* የ10፥20 ማብ ይመ።

4፥7 *በምንጠራው ጊዜ ... ለእኛ ቅርብ እንደ ሆነ፤* እስራኤላውያን ዘወትር በጸሎት ወደ እግዚአብሔር የመቅረብ ዕድል ነበራቸው። የእግዚአብሔር ህልዎት በሰፈሩ መኻል ለመኻል በተተከለው የመገናኛ ድንኳንና በድንኳኑም ላይ ባረፈው የደመና ዐምድ ተመስሎአል (ዘፀ 40፥34-38፤ ዘኍ 23፥21 ይመ)።

4፥9 *ለልጆቻችሁ ... አስተምሯቸው፤* ቍ 10፤ 11፥19 ይመ፤ ከዘፀ 12፥26-27 ጋር ያነጻጽሩ።

4፥10-14፤ ዘፀ 19-24 ይመ።

የቆማችሁበትን ዕለት አስታውሱ። [11]ተራራው በጥቍር ደመናና በድቅድቅ ጨለማ ተውጦ ሳለ ነበልባሉ ሰማይ እስከሚደርስ ድረስ በተቃጠለ ጊዜ መጥታችሁ ከተራራው ግርጌ ቆማችሁ። [12]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በእሳቱ ውስጥ ሆኖ ተናገራችሁ፤ እናንተም የቃሉን ድምፅ ሰማችሁ፤ መልክ ግን አላያችሁም፤ ድምፅ ብቻ ነበርና። [13]እርሱ ኪዳኑን ይኸውም እንድትከተሏቸው ያዘዛችሁን ዐሥርቱን ትእዛዛት ዐወጀላችሁ፤ ከዚያም በሁለት የድንጋይ ጽላቶች ላይ ጻፋቸው፤ [14]ዮርዳኖስን ተሻግራችሁ በምትወርሷት ምድር ውስጥ የምትከተሏቸውን ሥርዐትና ሕግ እንዳስተምራችሁ በዚያን ጊዜ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) አዘዘኝ።

## ጣዖትን ማምለክ ስለ መከልከሉ

[15]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በኮሬብ ተራራ ላይ በእሳት ውስጥ በተናገራችሁ ቀን ምንም ዐይነት መልክ ከቶ አላያችሁም፤ ስለዚህ ለራሳችሁ ተጠንቀቁ፤ [16]ይኸውም እንዳትረክሱ፣ በወንድ ወይም በሴት መልክ በማናቸውም ዐይነት ምስል የተቀረጸ ጣዖት ለራሳችሁ እንዳታበጁ፣ [17]ወይም በምድር ላይ የሚኖር የማናቸውንም እንስሳ ወይም በአየር ላይ የሚበር የማናቸውንም ወፍ፣ [18]ወይም በደረቱ የሚሳብ የማናቸውንም ፍጡር ወይም በውሃ ውስጥ የሚኖር የማናቸውንም ዓሣ ምስል እንዳታደርጉ ነው። [19]ወደ ሰማይ ቀና ብለህ ፀሓይን፣ ጨረቃንና ከዋክብትን፣ የሰማይ ሰራዊትንም ሁሉ በምትመለከትበት ጊዜ፣ ወደ እነርሱ እንዳትሳብና እንዳትሰግድላቸው፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከሰማይ በታች ላሉ ሕዝቦች ሁሉ ድርሻ አድርጎ የሰጣቸውንም ነገሮች እንዳታመልክ ተጠንቀቅ፤ [20]እናንተን ግን ልክ ዛሬ እንደ ሆናችሁት ሁሉ ርስቱ ትሆኑለት ዘንድ፣ *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እናንተን ከብረት ማቅለጫ ምድጃ፣ ከግብፅ አውጥቶ አመጣችሁ።

[21]በእናንተም ምክንያት እግዚአብሔር እኔን ተቈጣኝ፤ የርዳኖስንም እንዳልሻገርና *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ ወደ ሚሰጣችሁ ወደ መልካሚቱ ምድር እንዳልገባ ማለ። [22]እኔም በዚህች ምድር እሞታለሁ፤ ዮርዳኖስን አልሻገርም፤ እናንተ ግን ልትሻገሩ ነው፤ ያችንም መልካም ምድር ትወርሳላችሁ። [23]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከእናንተ ጋር የገባውን ኪዳን እንዳትረሱ ተጠንቀቁ፤ *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የከለከለውን ጣዖት በማናቸውም ዐይነት መልክ ለራሳችሁ አታብጁ። [24]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚባላ እሳት ቀናተኛም አምላክ (ኤሎሂም) ነውና።

[25]ልጆችንና የልጅ ልጆችን ከወለዳችሁና በምድሪቱም ላይ ለረጅም ጊዜ ከኖራችሁ በኋላ ራሳችሁን በማርከስ ማንኛውንም ዐይነት ጣዖት ብታበጁ፣ *በአምላካችሁም* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ክፉት በማድረግ ለቍጣ ብታነሣሡት፣ [26]ዮርዳኖስን ተሻግራችሁ ከምትወርሷት ምድር ላይ ፈጥናችሁ እንደምትጠፉ በዚህ ቀን ሰማይንና ምድርን በእናንተ ላይ ምስክሮች አድርጌ እጠራለሁ፣ በዚያ ቦታ ብዙ ዘመን አትኖሩም፤ ፈጽሞ ትጠፋላችሁ። [27]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እናንተን በአሕዛብ መካከል ይበትናችኋል፤ እግዚአብሔር በሚበትናችሁ አሕዛብ መካከል የምትተርፉት ጥቂቶቻችሁ ብቻ ናችሁ። [28]እዚያም፣ ማየት ወይም መስማት ወይም መብላት ወይም ማሽተት በማይችሉ በሰው እጅ በተሠሩ የእንጨትና የድንጋይ አማልክት ታመልካላችሁ። [29]ነገር ግን እዚያም ሆናችሁ *አምላካችሁን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) በፍጹም ልባችሁና በፍጹም ነፍሳችሁ ብትፈልጉት ታገኙታላችሁ። [30]ስትጨነቅና ይህ ሁሉ ነገር ሲደርስብህ ያን ጊዜ፣ በኋለኞቹ ዘመናት ወደ አምላክህ ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ትመለ

4፥11 ዘፀ3፥1፤ 19፥9፡17፡18፤ መዝ18፥11፤97፥2
4፥12 ዘፀ19፥9፤ 20፥22፤ዘዳ5፥4፡22፤ ዮሐ5፥37፤ማቴ3፥17፤ ዕብ12፥19
4፥13 ዘፀ24፥12፤ ዘዳ9፥9፤ሮሜ9፥4
4፥14 ዘፀ21፥1
4፥15 ዘፀ3፥1፤ ኢሱ23፥11፤ ኢሳ40፥18፤41፥22-24፤ ሚል2፥15
4፥16 ዘፍ6፥11-12፤ ዘፀ20፥4-5፤ዘዳ9፥12፤ 31፥29፤32፥5፤ መሳ2፥19፤ሮሜ1፥23
4፥17 ሮሜ1፥23
4፥19 ዘፍ1፥16፤ 2፥1፤37፥9፤ዘኍ25፥3፤ ዘዳ13፥5፤17፥3፤2ነገ2 3፥11፤ኤር8፥2፤43፥1 3፤ሕዝ8፥16፤ ኢዮ31፥26፤ ሮሜ1፥25
4፥20 ዘፍ17፥7፤ ዘፀ1፥13፤3፥10፤8፥22፤ 34፥9፤ቲቶ2፥14
4፥21 ዘኍ20፥12፤ ዘዳ1፥37
4፥22 ዘኍ27፥13-14፤ ዘዳ3፥25
4፥23 ቍ9፤ ዘፀ20፥4
4፥24 ዘፀ15፥7፤ 19፥18፤20፥5፤ ዕብ12፥29
4፥25 ቍ16፡23፤ 1ነገ11፥6፤15፥26፤ 16፥25፡30፤2ነገ17፥2፡ 17፤21፥2
4፥26 ዘፍ31፥50፤ ዘዳ6፥15፤7፥4፤ 30፥18-19፤31፥28፤ 32፥1፤መዝ50፥4፤ ምሳ14፥5፤ኢሳ1፥2፤ 34፥1፤ኤር6፥19፤ ሚክ6፥2፤
4፥27 ዘሌ26፥33፤ ዘዳ28፥36፡64፤29፥28፤ 1ነገ8፥46፤2ነገ17፥6፤ መዝ44፥11፤106፥27፤ ኢሳ17፥6፤21፥17፤ ኤር3፥8፤ሚክ1፥16፤ አብ1፥5
4፥28 ዘዳ13፥2፤ 28፥36፡64፤29፥17፤1ሳሙ26፥19፤መዝ115፥4-8፤ 135፥15-18፤ኢሳ8፥19፤26፥14፤44፥17-20፤ኤር5፥19፤16፥13፤ ሐሥ19፥26፤ራእ9፥20
4፥29 ዘዳ6፥5፤30፥1-3፡10፤1ሳሙ7፥3፤ 13፥12፤ 1ነገ8፥48፤ 2ነገ13፥4፤2ዜና7፥14፤15፥4፤33፥12፤ መዝ78፥34፤119፥58፤ኢሳ45፥19፡22፤55፥6፤ኤር26፥19፤29፥13፤ ዳን9፥13፤ሆሴ3፥5፤አሞ5፥4፤
4፥30 ዘሌ26፥41፤ዘዳ30፥2፤ 31፥17፡21፡29፤ 1ነገ8፥48፤ኢዩ1፥9፤መዝ4፥1፤18፥1፤46፥1፤59፥16፤ 107፥6፤ኤር3፥1፡12፡22፤4፥1፤18፥11፤ 23፥20፤ሆሴ3፥5፤ኢዩ2፥12፤ ዕብ1፥2

4፥10 *አስታውሱ፤* እግዚአብሔር በቀደመው ዘመን እስራኤልን እንዴት እንደታደገ በተለይም ከግብፅ ባርነት እንዴት እንዳወጣ ሕዝቡ መለስ ብሎ እንዲያስታውስ የቀረበው መለኮታዊ ጥሪ በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ተደጋግሞ የተወሳ መሪ ሐሳብ ሲሆን (5፥15፤ 7፥18፤ 8፥2፡18፤ 9፥7፡27፤ 11፥2፤ 15፥15፤ 16፥3፡12፤ 24፥9፡18፡22፤ 25፥17)፣ ይህም በ32፥7 ላይ፣ "የጥንቱን ዘመን አስታውስ" በሚለው አገላለጽ ተጠቃልሎአል።

4፥12 *መልክ ግን አላያችሁም፤* ቍ 15 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 20፥4 ማብ ይመ። "እግዚአብሔር መንፈስ ነው" (ዮሐ 4፥24 ይመ፤ ከኢሳ 31፥3 ጋር ያነጻጽሩ)።

4፥13 *ኪዳኑን ... ዐሥርቱን ትእዛዛት፤* የዘፀ 20፥1፤ 34፥28 ማብ ይመ። *ሁለት የድንጋይ ጽላቶች፤* የዘፀ 31፥18 ማብ ይመ።

*4፥15-18፤* የዘፀ 20፥4 ማብ ይመ።

4፥19 *ወደ እነርሱ እንዳትሳብ፤* ከብዙ ዘመን በኋላ የይሁዳ ንጉሥ እንደ ሆነው ማለት ነው (2ነገ 23፥5)።

4፥20 *ከብረት ማቅለጫ ምድጃ፤* እስራኤላውያን በግብፅ ምድር ያሳለፉት ጊዜ የመከራ፣ የፈተናና የመጥሪያ ጊዜ እንደ ነበረ ያመለክታል (1ነገ 8፥51፤ ኤር 11፥4 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ 48፥10 ይመ)።

4፥21 *በእናንተም ምክንያት፤* የ1፥37 ማብ ይመ።

4፥24 *የሚባላ እሳት፤* 9፥3 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 24፥17 ማብ ይመ። *ቀናተኛ አምላክ፤* 5፥9፤ 6፥15 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 20፥5 ማብ ይመ።

4፥25 *በምድሪቱ ላይ ... ከኖራችሁ በኋላ፤* የእስራኤላውያን ዐመፅ፣ በዚህም ምክንያት ከምድሪቱ ተነቃቅለው መሰደድ፣ ከዚያም በኀጢአታቸው ተጸጽተው ንስሓ በመግባት እንደገና ወደ ምድሪቱ መመለስ በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ጉልቶ የሚገኝ ሐሳብ ነው (ለምሳሌ በም 27-28 ላይ ያለውን የበረከትና የመርገም ዝርዝር ይመ)።

4፥26 *ሰማይና ምድርን ... ምስክሮች አድርጌ፤* የ30፥19፤ የመዝ 50፥1፤ የኢሳ 1፥2 ማብ ይመ።

4፥27 *ይበትናችኋል፤* የ28፥64 ማብ ይመ።

4፥29 *በፍጹም ልባችሁና፣ በፍጹም ነፍሳችሁ፤* ሙሉ በሙሉ መሰጠትን ያመለክታል። ሐረጉ የእግዚአብሔር ሕዝብ አምላኩን እንዴት መሻት እንዳለበት የሚያመለክት ብቻ ሳይሆን፣ እንዴት መፍራት፣ መታዘዝ፣ መውደድና ማገልገል እንዳለበት ጭምር የሚያሳይ ነው (6፥5፤ 10፥12፤ 11፥13፤ 13፥3፤ 30፥6)፤ ከዚህም በተጨማሪ ሕዝቡ ከአምላኩ መንገድ ዘወር ባለ ጊዜ እንዴት ተመልሶ ኅብረት መፍጠርና ራሱን መስጠት እንደሚችል ያመለክታል (26፥16፤ 30፥2፡10)።

ሳለህ፣ ትታዘዝለታለህም። [31]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) *መሐሪ* አምላክ (ኤሎሂም) ነውና፣ አይተውህም ወይም አያጠፋህም፤ ወይም ደግሞ ለአባቶችህ በመሐላ ያጸናላቸውን ቃል ኪዳን አይረሳም።

### *እግዚአብሔር* አምላክ (ያህዌ ኤሎሂም) ነው

[32]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሰውን በምድር ላይ ከፈጠረበት ቀን ጀምሮ እናንተ ከመኖራችሁ በፊት ስለ ነበረው የቀድሞ ዘመን ጠይቁ፤ ከአንዱ የሰማይ ጫፍ እስከ ሌላው የሰማይ ጫፍ ድረስ ጠይቅ፤ እንደዚህ ያለ ታላቅ ነገር ከቶ ተደርጎ ወይስ እንደዚህ ዐይነት ነገር ከቶ ተሰምቶ ያውቃልን? [33]ከእሳት ውስጥ የእግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ድምፅ እንደ እናንተ የሰማና በሕይወት የኖረ ከቶ ሌላ ሕዝብ አለን? [34]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በዐይናችሁ እያያችሁ ለእናንተ በግብፅ እንዳደረገው ሁሉ በፈተና፣ በታምራዊ ምልክቶችና በድንቆች፣ በጦርነት፣ በጸናች እጅና በተዘረጋች ክንድ ወይም ቢታላቅና በአስፈሪ ሥራዎች ከሌላ ሕዝብ መካከል አንድን ሕዝብ የራሱ ለማድረግ የቻለ አምላክ አለን?

[35]*እግዚአብሔር* እርሱ አምላክ (ያህዌ ኤሎሂም) *መሆኑን*፣ ከእርሱም በቀር ሌላ አምላክ አለ *መኖሩን ታውቁ ዘንድ* እነዚህን ነገሮች እንድ ታዩ ተደረገ። [36]ሊገሥጽህ ድምፁን ከሰማይ እንድትሰማ አደረገ፤ በምድርም ላይ አስፈሪ እሳቱን አሳየህ፤ ከእሳቱም ውስጥ ቃሉን ሰማህ። [37]አባቶችህን ከመውደዱ የተነሣና ከእነ ርሱም በኋላ ዘራቸውን ስለ መረጠ፣ ከአንተ ጋር በመሆን በታላቅ ኀይሉ ከግብፅ አወጣህ፤ [38]ዛሬ እንደ ሆነው ሁሉ ከአንተ ይልቅ ታላ ቅና ብርቱ የሆኑትን አሕዛብ ከፊትህ በማስ ወጣት ወደ ምድራቸው አስገብቶህ ለአንተ ርስት አድርጎ ለመስጠት ነው።

[39]እንግዲህ በላይ በሰማይ፣ በታችም በምድር *እግዚአብሔር* እርሱ አምላክ (ያህዌ ኤሎሂም) *መሆኑን* ዛሬ ዕወቅ፤ በልብህም ያዘው፤ ሌላም የለም። [40]ለአንተና ከአንተም በኋላ ለልጆችህ መልካም እንዲሆንላችሁ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለዘላለም በሚሰጥህም ምድር ዕድሜህ እንዲረዝም፣ ዛሬ እኔ የማዝህን ሥርዐቱንና ሕግጋቱን ጠብቅ።

4፥31 ዘፀ34፥6፤ ዘሌ26፥44፡45፤ ዘዳ31፥6፡8፤ኢሱ1፥5፤ 1ነገ8፥57፤1ዜና28፥9፡ 20፤ነህ9፥31፤ መዝ9፥10፤27፥9፤ 71፥9፤111፥4፤ ኢሳ42፥16፤ዕብ13፥5
4፥32 ቍ7፤ ዘፍ1፥27፤ዘዳ28፥64፤ 30፥1፤32፥7፤ 2ሳሙ7፥23፤ ኢሳ45፥12፤ ኤር9፥16፤ማቴ24፥31
4፥33 ዘፀ20፥22፤ ዘዳ5፥24-26
4፥34 ዘፀ3፥20፤ 4፥17፤14፥30፤15፥11፤ ዘዳ5፥15፤6፥21፤7፥19፤ 15፥15፤26፥8፤29፥3፤ 34፥12፤1ዜና16፥12፤ መዝ9፥1፤40፥5፤45፥4፤ 65፥5፤ኢሳ7፥12፤ ኤር32፥20፤
4፥35 ቍ39፤ዘፀ 8፥10፤ዘዳ7፥9፤32፥4፡ 12፤1ሳሙ2፥2፤1ነገ8 ፥60፤2ነገ19፥19፤ኢ ሳ43፥10፤ማር12፥32
4፥36 ዘፀ19፥19፤ ዘዳ8፥5፤ዕብ12፥25፤
4፥37 ዘፀ3፥20፤ 33፥14፤ዘዳ7፥8፤10፥1 5፤23፥5፤33፥3፤መዝ4 4፥3፤ኤር31፥3፤ሆሴ1 1፥1፤ሚል1፥2፤2፥11
4፥38 ዘኍ34፥14-15፤ ዘዳ7፥1፤9፥5
4፥39 ቍ35፤ ዘፀ8፥10፤15፥11
4፥40 ቍ1፤ ዘፍ26፥5፤ዘፀ23፥26፤ ዘሌ22፥31፤ዘዳ5፥16፡ 29፤11፥1፤12፥25፤ መዝ105፥45፤ኢሳ3፥10፤ 48፥18፤ኤፌ6፥2-3
4፥42 ዘፀ21፥13
4፥43 ኢሱ21፥38፤ 1ነገ22፥3፤2ነገ8፥28፤ 9፥14
4፥46 ዘኍ21፥26
4፥48 ዘዳ2፥36፤ 3፥8፡9
5፥1 ዘፀ18፥20
5፥2 ዘፍ17፥9፤ ዘፀ3፥1፤19፥5፤ ኤር11፥2፤ዕብ9፥15፤ 10፥15-17
5፥3 ዘኍ26፥63-65፤ ዘዳ11፥2-7፤ዕብ8፥9

### የመማፀኛ ከተሞች

4፥41-43 ማመ - ዘኍ 35፥6-34፤ ዘዳ 19፥1-14፤ ኢሱ 20፥1-9

[41]በዚያን ጊዜ ሙሴ ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ ሦስት ከተሞችን ለየ፤ [42]ይኸውም የቈየ ጠላትነት ሳይኖር፣ በድንገት ባልጀራውን የገደለ ማናቸውም ሰው ሸሽቶ ከእነዚህ ከተሞች ወደ አንዲቱ በመሄድ ሕይወቱን ማትረፍ ይችል ዘንድ ነው። [43]ከተሞቹም በምድረ በዳው በከፍተኛ ቦታ ላይ የምትገኘው ቦሶር ለሮቤላውያን፣ በገለዓድ የምትገኘው ራሞት ለጋዳውያን፣ በባሳን ያለችው ጎላን ለምናሴያውያን ነበሩ።

### ስለ ሕጉ የተሰጠ ማብራሪያ

[44]ሙሴ በእስራኤላውያን ፊት የደነገገው ሕግ ይህ ነው። [45]ከግብፅ በወጡ ጊዜ ሙሴ ለእ ስራኤላውያን የሰጣቸው *መመሪያዎች*፣ ሥርዐ ቶችና ሕጎች እነዚህ ናቸው፤ [46]ይህም ከግብፅ በወጡ ጊዜ በሙሴና በእስራኤላውያን ድል በተደረገው፣ በሐሴቦን በነገሠው፣ በአሞራ ውያን ንጉሥ በሴዎን ምድር፣ ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ በቤተ ፌጎር አጠገብ ባለው ሸለቆ ውስጥ በነበሩበት ጊዜ ነው። [47]ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ ያለውን፣ የእርሱን ምድርና የባሳ ንን ንጉሥ የዐግን፣ የሁለቱን አሞራውያን ነገሥታት ምድር ርስት አድርገው ወሰዱ። [48]ይህም ምድር በአርኖን ሸለቆ ዳርቻ ካለው ከአሮዔር አንሥቶ እስከ ሴዎን[a] ተራራ ማለ ትም እስከ አርሞንዔም የሚደርስ ሲሆን፣ [49]በዮርዳኖስ ምሥራቅ ያለውን ዓረባን በሙሉና ከፈስጋ ተረተር በታች ያለውን የዓረባ ባሕር[†] ያጠቃልላል።

### ዐሥርቱ ትእዛዛት

5፥6-21 ተጓ ምብ - ዘፀ 20፥1-17

**5** ሙሴ እስራኤልን ሁሉ ጠርቶ እንዲህ አላቸው፤ "እስራኤል ሆይ፤ በዛሬዋ ዕለት በጆሮአችሁ የምነግራችሁን ሥርዐትና ሕግ ስሙ፤ አጥኗቸው፤ በጥንቃቄም ጠብቋቸው። [2]*አምላካ ችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በኮሬብ ከእኛ ጋር ቃል ኪዳን ገብቶአል። [3]እግዚአብሔር ይህን ቃል ኪዳን የገባውም ከአባቶቻችን ጋር ሳይሆን፣ ዛሬ እዚህ በሕይወት ከምንገኘው ከእኛ ከሁላችን

[a]48 የዕብራይስጡና የሱርስቱ ትርጒም፣ ሢርዮን ይለዋል (ዘዳ 3፥9 ይመ)

[†]49 ይኸውም የሙት ባሕር ነው።

4፥31 *በመሐላ ያጸናላቸውን ቃል ኪዳን፤* የዘፍ 21፥23፤ 22፥16፤ የዕብ 6፥13፡18 ማብ ይመ። በጥንት ዘመን ቃል ኪዳን የሚጋቡ ሁለት ወገኖች የገቡትን ቃል ባይፈጽሙ በራሳቸው ላይ ክፉ ነገር እንዲደርስ በመሐላ ያረጋግጡ ነበር (የዘፍ 15፥17 ማብ ይመ)።

4፥35 *ታውቁ ዘንድ፤* ቍ 10 ይመ። *ከእርሱ በቀር ሌላ አምላክ አለመኖሩን፤* ቍ 39፤ 5፥7፤ 6፥4 እና ማብ፤ 32፥39 ይመ። ሙሴ ለአንዱ አምላክ ያለው እምነት ፍጹምና የማያወላውል ነበር (የዘፍ 1፥1 ማብ ይመ)።

4፥37 *ከመውደዱ፤* ይህ ቃል በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ያለውን ፍቅር የሚያሳይ የመጀመሪያው ጥቅስ ነው። የ7፥8 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 5፥10፤ 7፥9፡13፤ 10፥15፤ 23፥5 ይመ። ባንጻሩም ሕዝቡ አምላኩን መውደድ እንዳለበት ያሳያል (የ6፥5 ማብ ይመ)።

4፥39፤ ቍ 35 እና ማብ ይመ።

4፥41-43፤ 19፥1-13፤ ዘኍ 35፥9-28፤ ኢሱ 20 ይመ።

4፥43 *ቦሶር፤* ከሙት ባሕር በስተ ሰሜን ምሥራቅ ማዕዘን 32 ኪ.ሜ. ያህል ርቃ የምትገኝ ከተማ ናት።

5፥1 *እስራኤል ሆይ፤ ... ስሙ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

5፥2 *በኮሬብ ከእኛ ጋር ቃል ኪዳን፤* የዘፀ 19፥5 ማብ ይመ። እግዚአብሔር በኮሬብ (በሲና) ተራራ ከእስራኤላውያን ጋር የገባውና አሁን እዚህ ላይ እንደገና የታደሰው ኪዳን እስራ ኤላውያን እግዚአብሔርን ብቻ አምላካቸው፣ ሕጉንና ሥርዐቱንም የሕይወታቸው መመሪያ እንዲያደርጉ ከእግዚአብሔር ጋር አስተ ሳስሮአቸዋል። በኪዳኑ መሠረት መኖር የእግዚአብሔርን በረከት ያወርድላቸዋል፤ ኪዳኑን አፍርሰው ቢገኙ ግን፣ "መርገም" የተባለው (ለምሳሌ 28፥15-20 ይመ) ቅጣት ያደርስባቸዋል። የሲናውን ኪዳን የሚሽር አዲስ ኪዳን እንደሚመሠረት በኤር 31፥31-34 አስቀድሞ ተነግሮአል (ዕብ 7፥22 ይመ፤ እንዲሁም ዕብ 8፥6-13፤ 10፥15-18 እና ማብ ይመ)።

5፥3 *ከአባቶቻችን ጋር ሳይሆን ... ከእኛ ከሁላችን ጋር፤* ቃል ኪዳኑ የተደረገው በሲና ተራራ ከተገኙት ጋር ቢሆንም፣ እነርሱ ሕዝቡን ሁሉ የሚወክሉ በመሆናቸው፣ ከእነርሱ በኋላ ከተነሣው ከእስራኤል ትውልድ ሁሉ ጋር የተደረገ ቃል ኪዳን

ጋር ነው። [4]እግዚአብሔር (ያህዌ) እናንተን በተራራው ላይ በእሳት ውስጥ ሆኖ ፊት ለፊት አነጋገራችሁ። [5]እናንተ ግን እሳቱን በመፍራት ወደ ተራራው ስላልወጣችሁ፣ በዚያን ጊዜ የእግዚአብሔርን (ያህዌ) ቃል ለእናንተ እነግራችሁ ዘንድ እኔ በእግዚአብሔርና (ያህዌ) በእናንተ መካከል ቆምሁ፤ እርሱም እንዲህ አለ፤

[6]"ከባርነት ምድር፣ ከግብፅ ያወጣሁህ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እኔ ነኝ።

[7]"ከእኔ በቀር[*] ሌሎች አማልክት አይሁኑልህ።

[8]በላይ በሰማይ፣ በታች በምድር ላይ፣ ባለው ወይም ከምድር በታች ውሃ ውስጥ በሚኖር በማንኛውም ዐይነት ምስል ለራስህ ጣዖትን አታብጅ፤

[9]እኔ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም)፣ የሚጠሉኝን ስለ አባቶቻቸው ኀጢአት እስከ ሦስትና እስከ አራት ትውልድ ድረስ ልጆቻቸውን የምቀጣ ቀናተኛ አምላክ ነኝና። ለእነርሱ አትስገድላቸው፤ ወይም አታምልካቸው። [10]ለሚወዱኝና ትእዛዛቴን ለሚጠብቁ ግን እስከ ሺህ ትውልድ ቸርነትንና ፍቅርን እገልጣለሁ።

[11]"እግዚአብሔር (ያህዌ) ስሙን በከንቱ የሚያነሣውን ሳይቀጣው አይቀርምና፤ የአምላክህን የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ስም በከንቱ አታንሣ።

[12]"አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባዘዘህ መሠረት የሰንበትን ቀን ቀድሰህ አክብረው። [13]ስድስት ቀን ሥራ፤ ተግባርህንም ሁሉ አከናውን። [14]ሰባተኛው ቀን ግን የአምላክህ የእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ሰንበት ነው። በዚህም ቀን አንተም ሆንህ ወንድ ወይም ሴት ልጅህ፣ ወንድ አገልጋይህም ሆነ ሴት አገልጋይህ በሬህ፣ አህያህ ወይም ማናቸውም እንስሳህ፣ ወይም ደጅህ በደጅህ ያለ እንግዳ ምንም ዐይነት ሥራ አትሥሩ። ይህም አንተ እንዳረፍህ ሁሉ ወንድ አገልጋይህም ሆነ ሴት አገልጋይህ እንዲያርፉ ነው። [15]በግብፅ ሳለህ አንተም ባሪያ እንደ ነበርህ፣ ከዚያም አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በጸናች እጅና በተዘረጋ ክንድ እንዳወጣህ አስታውስ፤ ስለዚህ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሰንበትን ቀን ታከብረው ዘንድ አዘዘህ።

[16]"አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ ምድር ላይ ዕድሜህ እንዲረዝምና መልካም እንዲሆንልህ፣ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባዘዘህ መሠረት አባትህንና እናትህን አክብር።

[17]"አትግደል።

[18]"አታመንዝር።

[19]"አትስረቅ።

[20]"በባልንጀራህ ላይ በሐሰት አትመስክር።

[21]"የባልንጀራህን ሚስት አትመኝ። በባልንጀራህ ቤትም ሆነ በመሬቱ፣ በወንድ ሆነ በሴት አገልጋዩ፣ በበሬውም ሆነ በአህያው ወይም የእርሱ በሆነው ነገር ላይ ዐይንህን አትጣል።"

[22]እግዚአብሔር (ያህዌ) በተራራው ላይ በእሳቱ፣ በደመናውና በድቅ ድቅ ጨለማ ውስጥ ለማኅበራችሁ ሁሉ በከፍተኛ ድምፅ የተናገራችሁ ትእዛዛቱ እነዚህ ናቸው፤ የጨመረውም ሌላ የለም፤ ትእዛዛቱንም በሁለት የድንጋይ ጽላቶች ላይ ጽፎ ሰጠኝ።

[23]ተራራው በእሳት ሲቃጠል፣ ከጨለማው ውስጥ ድምፁን በሰማችሁ ጊዜ እናንተ የየነገዶቻችሁ አለቆችና ሽማግሌዎቻችሁም በሙሉ ወደ እኔ ዘንድ መጣችሁ፤ [24]እንዲህም አላችሁ፤ "አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ክብሩንና ግርማውን አሳይቶናል፤ ከእሳቱም ውስጥ ድምፁን ሰምተናል። እግዚአብሔር አነጋግሮትም እንኳ፣ ሰው በሕይወት ሊኖር እንደሚችል በዛሬው ቀን አይተናል። [25]ከእንግዲህ የአምላካችንን የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ድምፅ ብንሰማ እንሞታለን፤ ይህችም ታላቅ እሳት ፈጽማ ታጠፋናለች፤ ታዲያ ለምን እንሙት? [26]ለመሆኑ ከእሳት ውስጥ ሆኖ ሲናገር እኛ እንደ ሰማነው ሁሉ፣ የሕያው እግዚአብሔርን (ኤሎሂም) ድምፅ ሰምቶ በሕይወት ለመኖር የቻለ ከሥጋ ለባሽ ማን አለ? [27]አንተ ቅረብ፤ አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚለውን ሁሉ አዳምጥ፤ ከዚያም አምላካችን እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚነግርህን ሁሉ ንገረን፤ እኛም እንሰማለን፤ እናደርገዋለንም።"

[28]ይህን ስትነግሩኝ እግዚአብሔር (ያህዌ) ሰማ፤ እግዚአብሔርም (ያህዌ) አለኝ፤ "ይህ ሕዝብ ምን እንዳለህ ሰምቻለሁ፤ ያሉትም ሁሉ መልካም ነው። [29]ታዲያ ለእነርሱም ሆነ ለልጆቻቸው

5፥4 ዘኍ14፥14፤ ዘዳ4፥12፤ዘፀ19፥18
5፥5 ዘፍ3፥10፤ ገላ3፥19፤ዕብ12፥18-21
5፥6 ዘፀ13፥3፤ 29፥46፤ዘሌ26፥1፤ ዘዳ6፥4፤መዝ81፥10
5፥8 ዘሌ26፥1፤ ዘዳ4፥15-18፤ መዝ78፥58፤97፥7
5፥9 ዘፀ34፥7፤ ዘኍ26፥11፤10፥35፤ 14፥18
5፥10 ዘፀ34፥7፤ ዘኍ14፥18፤ዘዳ7፥9፤ ነህ1፥5፤ኤር32፥18፤ ዳን9፥4
5፥11 ዘሌ19፥12፤ ዘዳ10፥20፤ መዝ139፥20፤ ማቴ5፥33-37
5፥12 ዘፀ16፥23-30፤ 31፥13-17፤ ማር2፥27-28
5፥14 ዘፍ2፥2፤ ኤር17፥21፥24፤ 34፥9-11፤ኢዮ31፥13፤ ማቴ12፥2፤ማር2፥27፤ ዕብ4፥4
5፥15 ዘፍ15፥13፤ ዘፀ6፥1፤ዘዳ4፥34፤ መዝ108፥6፤ ኤር32፥21፤
5፥16 ዘፀ21፥17፤ ዘሌ19፥3፤ዘዳ4፥40፤ 11፥9፤ምሳ3፥1-2፤ ሕዝ22፥7፤ሚል1፥6፤ ማቴ15፥4፤19፥19፤ ማር7፥10፤10፥19፤ ሉቃ18፥20፤ኤፌ6፥2-3
5፥17 ዘፍ9፥6፤ ዘሌ24፥17፤መክ3፥3፤ ኤር40፥15፤41፥3፤ ማቴ5፥21-22፤ 19፥19፤ማር10፥19፤ ሉቃ18፥20፤ሮሜ 13፥9፤ያዕ2፥11
5፥18 ዘሌ20፥10፤ ማቴ5፥27-30፤ 19፥18፤ማር10፥19፤ ሉቃ18፥20፤ሮሜ13፥9፤ ያዕ2፥11
5፥19 ዘሌ19፥11፤ ማቴ19፥19፤ ማር10፥19፤ ሉቃ18፥20፤ሮሜ13፥9
5፥20 ዘፀ23፥1፤ ማቴ19፥18፤ ማር10፥19፤ ሉቃ18፥20
5፥21 ሮሜ7፥7፤13፥9
5፥22 ዘፀ20፥21፤ 24፥12

5፥23 ዘፀ3፥16 5፥24 ዘፀ19፥19፤ ዘዳ3፥24፤4፥34፥8፥5፤11፥2፤ ኢሳ53፥4፤ 5፥25 ዘፀ20፥18-19፤ ዘዳ18፥16፤ዕብ12፥19
5፥26 ዘፀ33፥20፤ ዘዳ4፥33፤መሳ6፥22-23፤ 13፥22፤ኢሳ6፥5
5፥27 ዘፀ19፥8፤ 24፥7 5፥28 ዘዳ18፥17 5፥29 ቈ33፥ ዘዳ4፥1፤40፤12፥25፤22፥7፤ኢሳ22፥5፤ መዝ78፥7፤81፥8፥13፤

[*]7 ወይም ፣ ከፊቴ ተብሎ መተርጐም ይችላል።

ተደርጎ ይቈጠራል።

*5፥5፤* ቍ 23-26፤ ዘፀ 20፥18-21 ይመ።

*5፥6-21፤* ዐሥርቱ ትእዛዛት እስራኤላውያን ከእግዚአብሔር ጋር ላላቸው ግንኙነት መሠረትና እምብርት ናቸው። ትእዛዛቱ ከተሰጡበት ጊዜ ጀምሮ በሰው ልጅ ታሪክ ላይ ያመጡት ለውጥ በቀላሉ የሚታይ አይደለም። እነዚህ ትእዛዛት በማናቸውም ኅብረተ ሰብ ውስጥ ለምናገኛቸው የምግባር መመሪያዎች መሠረት ሲሆኑ፣ እውነተኛውና ብቸኛው አምላክ እምነትን፣ አምልኮንና የዕለት ተዕለት ኑሮን አስመልክቶ ከሕዝቡ የሚፈልገው ምን እንደሆነ በእነዚሁ ትእዛዛት ላይ ተጠቃሎአል (የዘፀ 20፥3-17 ማብ ይመ)።

5፥12 *አምላክህ እግዚአብሔር ባዘዘህ መሠረት፤* ይህ ሐረግ በዘፀአት መጽሐፍ ተጓዳኝ ክፍል ላይ (ዘፀ 20፥8) ተጠቅሶ ባይገኝም፣ ከ40 ዓመት በፊት የተሰጡት ዐሥርቱ ትእዛዛት መግኛቸው እግዚአብሔር መሆኑን ሕዝቡን ያሳስባል (ቍ 15-16 ይመ)።

5፥14 *ወንድ አገልጋይህም ሆነ ሴት አገልጋይህ ... ምንም ዐይነት ሥራ አትሥሩ፤* የዘፀ 20፥10 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ቍ 15 ይመ።

5፥15 *አስታውስ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

*5፥16-21፤* ይህ በአዲስ ኪዳን በአብዛኛው ተጠቅሶ የምናገኘው የዐሥርቱ ትእዛዛት ክፍል ነው።

*5፥20፤* 19፥18-19 ይመ።

5፥22 *ትእዛዛቱ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ቃላቱ" ማለት ነው (የዘፀ 20፥1 ማብ ይመ)። *ሁለት የድንጋይ ጽላቶች፤* የዘፀ 31፥18 ማብ ይመ።

5፥25 *እንሞታለን፤* የዘፍ 16፥13፤ 32፥30 ማብ ይመ።

5፥27 *እንሰማለን፤ እናደርገዋለንም፤* የዘፀ 19፥8 ማብ ይመ።

ለዘላለም መልካም እንዲሆንላቸው፣ እኔን እንዲፈሩና ሁልጊዜ ትእዛዞቼን ሁሉ እንዲጠብቁ እንደዚህ ያለ ልብ ቢኖራቸው ምናለ!

[30]ሂደህ ወደየድንኳናቸው እንዲመለሱ ንገራቸው። [31]አንተ ግን እንዲወርሷት በምሰጣቸው ምድር እንዲጠብቋቸው የምታስተምራቸውን ትእዛዞች፣ ሥርዐቶችና ሕጎች ሁሉ እንድሰጥህ እዚሁ ከእኔ ዘንድ ቈይ።"

[32]እንግዲህ *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) ያዘዛችሁን ለመፈጸም ተጠንቀቁ፤ ቀኝም ግራም አትበሉ። [33]በምትወርሷት ምድር በሕይወት ለመኖር እንድትችሉ፣ መልካም እንዲሆንላችሁና ዕድሜያችሁም እንዲረዝም፣ *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) ባዘዛችሁ መንገድ ሁሉ ሂዱ።

## *አምላክህን* እግዚአብሔርን ውደድ

**6** ዮርዳኖስን ተሻግራችሁ በምትወርሷት ምድር እንድትጠብቁት አስተምራችሁ ዘንድ *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) የሰጠኝ ትእዛዝ፣ ሥርዐትና ሕግ ይህ ነው፤ [2]ይኸውም፣ የምሰጣችሁን ሥርዐቱንና ትእዛዙን ሁሉ በመጠበቅ፣ ዕድሜያችሁ እንዲረዝም፣ አንተ፣ ልጆችህና ከእነርሱ በኋላ የሚመጡት ልጆቻቸው በሕይወት ዘመናችሁ ሁሉ *አምላካችሁን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሉሂም) ትፈሩት ዘንድ ነው። [3]እንግዲህ እስራኤል ሆይ ስማ፤ የአባቶችህ *አምላክ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) በሰጠህ ተስፋ መሠረት፣ ማርና ወተት በምታፈሰው ምድር መልካም እንዲሆንልህና እጅግ እንድትበዛ፣ ትእዛዙንም ትጠብቅ ዘንድ ጥንቃቄ አድርግ።

[4]እስራኤል ሆይ ስማ፤ *አምላካችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) አንድ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ነው[ኀ]። [5]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሉሂም) በፍጹም ልብህ፣ በፍጹም ነፍስህ፣ በፍጹም ኀይልህ ውደድ። [6]ዛሬ የምሰጥህን እነዚህን ትእዛዛት በልብህ ያዝ። [7]ለልጆችህም አስጠናቸው፤ በቤትህ ስትቀመጥ፣ በመንገድም ስትሄድ፣ ስትተኛና ስትነሣም ስለ እነርሱ ተናገር። [8]በእጅህ ላይ ምልክት አድርገህ እሰራቸው፤ በግንባርህም ላይ ይሁኑ። [9]በቤትህ መቃኖች በግቢህም በሮች ላይ ጻፋቸው።

[10]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) ለአንተ ለመስጠት ለአባቶችህ ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ ወደ ማለላቸው ምድር ሲያስገባህ፣ በዚያም ያልሠራሃቸውን ታላላቅና ያማሩ ከተሞችን፣ [11]የራስህ ባልነበሩ መልካም ነገሮች ሁሉ የተሞሉ ቤቶችን ያልቈፈርሃቸውን የውሃ ጕድጓዶች፣ ያልተከልሃቸውን የወይን ተክሎችና የወይራ ዛፎች ሲሰጥህና በልተህም ስትጠግብ፣ [12]ከባርነት ምድር ከግብፅ ያወጣህን *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) እንዳትረሳ ተጠንቀቅ!

[13]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሉሂም) ፍራ፤ እርሱን ብቻ አገልግል፤ በስሙም ማል። [14]በዙሪያህ ያሉ ሕዝቦች የሚያመልኳቸውን ሌሎች አማልክት አትከተል፤ [15]ምክንያቱም በመካከልህ ያለው *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) ቀናተኛ አምላክ (ኤሉሂም) ስለ ሆነ፣ በአንተም ላይ ቍጣው ስለሚነድ፣ ከምድር ገጽ ያጠፋሃል። [16]በማሳህ እንዳደረጋችሁት *አምላካችሁን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሉሂም) አትፈታተኑት። [17]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሉሂም) የሰጣችሁን ትእዛዞች፣ መመሪያዎችና ሥርዐቶች በጥንቃቄ ጠብቁ። [18]መልካም እንዲሆንልህና *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለአባቶችህ በመሐላ ተስፋ የሰጣቸውን መልካሚቱን ምድር ገብተህ እንድትወርሳት፣ በ*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ቀናና መልካም የሆነውን አድርግ፤ [19]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በተናገረው መሠረትም ጠላቶችህን ሁሉ ከፊትህ ታስወጣለህ። [20]በሚመጡት ዘመናት ልጅህ፣

5፥31 ዘፀ24፥12
5፥32 ዘዳ4፥29፤ 10፥12፤17፥11:20፤ 28፥14፤ኢሱ1፥7፤ 1ነገ15፥5፤2ነገ22፥2፤ ምሳ4፥27
5፥33 ቍ29፤ ኢሳ3፥10፤ኤር7፥23፤ 38፥20፤ሉቃ1፥6፤
6፥2 ዘፍ26፥5፤ ዘፀ20፥12:20፤ዘዳ4፥9፤ 1ሳሙ12፥24፤
6፥3 ዘፍ15፥5፤ ዘፀ3፥8፤13፥5፤19፥5፤ ዘዳ5፥33፤32፥13-14፤
6፥4 ዘዳ4፥35:39፤ ነህ9፥6፤መዝ86፥10፤ ኢሳ44፥6፤ዘካ14፥9፤ ማር12፥29፤ ዮሐ10፥30፤1ቆሮ8፥4፤ ኤፌ4፥6፤ያዕ2፥19
6፥5 ዘዳ4፥29፤ 10፥12፤11፥1:22፤ ኢሱ22፥5፤ 1ሳሙ12፥24፤ ማቴ22፥37፤ ማር12፥30፤ ሉቃ10፥27፤
6፥6 ቍ8፤ዘዳ11፥18፤ 30፥14፤32፥46፤ ምሳ3፥3፤መዝ26፥2፤ 37፥31፤40፥8፤ 119፥11፤ኢሳ51፥7፤ ኤር17፥1፤31፥33፤ ሕዝ40፥4
6፥7 ዘዳ4፥9፤11፥19፤ ምሳ22፥6፣ኤፌ6፥4
6፥8 ቍ6፤ዘፀ13፥9፤ ማቴ23፥5
6፥9 ዘዳ11፥20
6፥10 ዘፍ11፥4፤ ዘዳ12፥29፤19፥1፤ ኢሱ24፥13፤ መዝ105፥44
6፥11 ዘሌ26፥5፤ ዘዳ8፥10፤14፥29፤ 31፥20ኤር2፥13፤
6፥12 ዘዳ4፥9:23፤ 2ነገ17፥38፤ መዝ44፥17፤78፥7፤103፥2
6፥13 ዘፀ20፥7፤ ዘዳ13፥4፤1ሳሙ7፥3፤ 20፥3፤መዝ33፥8፤ 34፥9፤ ኤር44፥10፤ማቴ4፥10፤5፥33፤ ሉቃ4፥4:8፤
6፥15 ዘዳ4፥24፤ 5፥9 6፥16 ዘፀ17፥2፤ማቴ4፥7፤ሉቃ4፥12
6፥17 ዘሌ26፥3፤ ዘዳ11፥22፤መዝ119፥4: 56:100:134:168
6፥18 ዘዳ4፥40፤ 2ነገ18፥6፤ኢሳ36፥7፤ 38፥3
6፥19 ዘፀ23፥27፤ ኢሱ21፥44፤ መዝ78፥53፤107፥2፤136፥24
6፥20 ዘፀ10፥2

[ኀ]4 ወይም፣ *እግዚአብሔር አምላካችን ነው፤ እግዚአብሔር አንድ ነው ወይም እግዚአብሔር አምላካችን ነው፤ እግዚአብሔር ብቻውን*

6፥2 *ዕድሜአችሁ እንዲረዝም፤* 4፥40፤ 5፥16:33 ይመ። እግዚአብሔርን በመታዘዝና ሕጋጋቱንም በመጠበቅ፣ እያንዳንዱ እስራኤላዊ በምድሪቱ ለረዥም ዘመን ይኖራል፤ ሕዝቡም በአጠቃላይ ለረጅም ዘመን በምድሪቱ በሰላም ይኖራል። *እግዚአብሔርን ትፈሩት ዘንድ፤* የዘፍ 20፥11 ማብ ይመ።

6፥3-4 *እስራኤል ሆይ ስማ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

6፥3 *ማርና ወተት በምታፈሰው ምድር፤* የዘፀ 3፥8 ማብ ይመ። ይህ ሐረግ ከዘፀአት እስከ ዘዳግም 14 ጊዜ፣ በሌሎቹ የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ደግሞ 5 ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል (በተለይ 32፥13-14 ይመ)።

*6፥4-9፤* በዕብራይስጥ፣ 'ሽማ' በመባል ይታወቃል፤ ትርጕሙም "ስማ" ማለት ነው። ይህ ክፍል የአይሁድ የእምነት መግለጫና ሃይማኖተኞች በየዕለቱ የሚደግሙት ጸሎት ሆኖአል (ማቴ 22፥37-38፤ ማር 12፥29-30፤ ሉቃ 10፥27 ይመ)።

6፥4 *እግዚአብሔር ... አንድ እግዚአብሔር ነው፤* በተለይ የበኣል አማልክትና ሌሎች አማልክት በበዙበት በከነዓንና በሌላ ስፍራ፣ እግዚአብሔር እርሱ ብቻ አምላክ መሆኑን ማወቅ መለኮት የሚገልጠው መረዳት ነው (ለምሳሌ መሳ 2፥11-13 ይመ)።

6፥5 *እግዚአብሔር ... ውደድ፤* እግዚአብሔርንና ሰውን መውደድ (ዘሌ 19፥18) የተመሠረተው፣ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ባለው ፍቅርና (1ዮሐ 4፥19-21) ራሱን ከሕዝቡ ጋር አንድ በማድረጉ ላይ ነው። የዚህ ዐይነቱ ፍቅር ፍጹምና ሁለንተናን መስጠትን ይጠይቃል (የ 4፥29፤ የኢሱ 22፥5 ማብ ይመ)።

6፥6 *ትእዛዛት በልብህ ያዝ፤* በተለይ፣ "አዲሱን ኪዳን" የሚያመለክት አገላለጽ ነው (ኤር 31፥33 ይመ)።

*6፥8-9፤* አይሁዳውያን ይህን አባባል ቃል በቃል በመተርጐም አሸንክታብ በግንባራቸውና በግራ ክንዳቸው ላይ ያስራሉ (የማቴ 23፥5 ማብ ይመ)። ከዚህም ሌላ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ ያለባቸውን ጽሕፈቶች በዕንጨት ወይም በብረት ሣጥን ውስጥ በማድረግ በበራቸው መቃን ላይ ያንጠለጥሉ ነበር። ይሁን እንጂ ይህ ክፍል ተምሳሌታዊ ትርጕም ሊኖረው እንደሚችል 11፥18-20፤ ዘፀ 13፥9:16 ይጠቁማሉ። የዘፀ 13፥9 ማብ ይመ።

*6፥10-12፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ አጽንዖት የሚሰጠው ሰዎች በጥረታቸው የሚያገኙት ነገር ሳይሆን፣ እግዚአብሔር የሚሠራው ሥራ ነው፤ ስለሆነም ሰዎች እግዚአብሔር ያደረገላቸውን በጎ ነገር ከቶ መዘንጋት የለባቸውም።

*6፥13፤* ኢየሱስ በሰይጣን በተፈተነ ጊዜ ይህን ጥቅስ በከፊል ጠቅሶታል (ማቴ 4፥10፤ ሉቃ 4፥8)። ሰይጣን ላቀረበለት ሌሎች ሁለት ፈተናዎች፣ ኢየሱስ ጠቅሶ መልስ የሰጠው ከዚሁ ከዘዳግም መጽሐፍ ነው (የቍ 16፤ 8፥3 ማብ ይመ)።

6፥15 *ቀናተኛ አምላክ፤* የዘፀ 20፥5 ማብ ይመ።

*6፥16፤* በማቴ 4፥7፤ ሉቃ 4፥12 ላይ ኢየሱስ በከፊል ጠቅሶታል። (የቍ 13 ማብ በተጨማሪ ይመ)። *በማሳህ እንዳደረጋችሁ፤* 9፥22፤ 33፥8 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 17፥7 ማብ ይመ።

*6፥20፤* ዘፀ 12፥26 እና ማብ ይመ።

"*አምላካችን* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ያዘዛችሁ የመመሪያዎቹ፣ የሥርዐቶቹና የሕጎቹ ትርጕም ምንድነው?" ብሎ በሚጠይቅህ ጊዜ፣ [21]እን ዲህ በለው፤ "እኛ በግብፅ የፈርዖን ባሮች ነበርን፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ግን በብርቱ እጅ ከግብፅ አወጣን:: [22]እኛ በዐይናችን እያየን *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ታላላቅና አስፈሪ የሆኑ ታምራዊ ምልክቶችና ድንቆችን በግብፅ፣ በፈር ዖንና በመላው ቤተ ሰዎቹ ላይ አደረገ:: [23]እኛን ግን ለአባቶቻችን በመሐላ ተስፋ ወደ ሰጣቸው ምድር ሊያስገባንና ሊሰጠን ከዚያ አወጣን:: [24]ዛሬ እንደ ሆነው ሁሉ ምን ጊዜም መልካም እንዲሆንልንና በሕይወት እንድንኖር ይህን ሥርዐት ሁሉ እንድንፈጽም፣ *አምላካ ችንንም* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) እንድንፈራ *እግዚ አብሔር* (ያህዌ) አዘዘን:: [25]እንግዲህ ይህን ሁሉ ሕግ እርሱ ባዘዘን መሠረት፣ *በአምላካችን* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ተጠንቅቀን ከጠ በቅን፣ ያ ለእኛ ጽድቃችን ይሆናል::"

## አሕዛብን ማስወጣት

**7** *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ልትወርሳት ወደምትገባባት ምድር በሚያመጣህና ብዙ ዎችን፣ ከአንተ የሚበልጡ ታላላቆችና ብር ቱዎች የሆኑትን ሰባቱን አሕዛብ:- ኬጢ ያውያንን፤ ጌርጌሳውያንን፣ አሞራውያንን፣ ከነዓናውያንን፣ ፌርዛውያንን፣ ኤዊያውያንንና ኢያቡሳውያንን ከፊትህ በሚያስወጣቸው ጊዜ፣ [2]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጅህ አሳልፎ በሰጠህና አንተም ድል ባደረግሃቸው ጊዜ፣ ሁሉንም ፈጽመህ ደምስሳቸው[1]፤ ከእነርሱ ጋር አትዋዋል፤ አትራራላቸውም:: [3]ከእነርሱ ጋር ጋብቻ አታድርግ፤ ሴት ልጆችህን ለወንድ ልጆቻቸው አትስጥ፤ ወይም ለወንድ ልጆችህ ሴት ልጆቻቸውን አታምጣ፤ [4]ምክንያቱም እኔን ከመከተል ልጆችህን መልሰው ሌሎችን አማልክት እንዲያመልኩ ስለሚያደርጉና ከዚ ህም የተነሣ *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ቍጣ በላይህ ነዶ፣ ፈጥኖ ስለሚያጠፋህ ነው:: [5]እንግዲህ በእነርሱ ላይ የምታደርጉት ይህ ነው፤ መሠ ዊያዎቻቸውን አፈራርሱ፤ የማምለኪያ ዐምዶቻ ቸውን[5] ሰባብሩ፤ የአሼራ ምስል ዐምዶቻቸውን ቍረጡ፤ ጣዖቶቻቸውንም በእሳት አቃጥሉ:: [6]አንተ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ቅዱስ ሕዝብ ስለ ሆንህ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የራሱ ሕዝብ፣ ርስትም እንድትሆንለት በምድር ላይ ከሚኖሩ ሕዝቦች ሁሉ መረጠህ::

[7]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እናንተን የወደዳችሁና የመረጣችሁ ከሌሎች ሕዝቦች በቍጥር ስለ በዛችሁ አይደለም፤ ቍጥራችሁማ ከሕዝቦች ሁሉ እጅግ አነስተኛ ነበር:: [8]ነገር ግን እና ንተን በብርቱ እጅ ያወጣችሁ፣ ከባርነት ምድርና ከግብፅ ንጉሥ ከፈርዖን መዳፍ የተ ቤዣችሁ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እናንተን ስለ ወደዳችሁና ለአባቶቻችሁ የማለላቸውን መሐላ ስለ ጠበቀ ነው:: [9]ስለዚህም *አምላክህ* እግዚአ ብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አምላክ (ኤሎሂም) *መሆኑን ዕወቅ*፤ እርሱ ለሚወዱትና ትእዛዞቹን ለሚጠብቁት የፍቅሩን ኪዳን እስከ ሺህ ትውልድ ድረስ የሚጠብቅ ታማኝ አምላክ (ኤሎሂም) ነው:: [10]ነገር ግን፣ የሚጠሉትን ዐይናቸው እያየ ይበቀላቸ ዋል፤ የሚጠሉትን ዐይናቸው እያየ ለመበቀል አይዘገይም::

[11]ስለዚህ በዛሬው ቀን የምሰጥህን ትእዛዙን፣ ሥርዐቱንና ሕግጋቱን ለመከተል ጥንቃቄ አድርግ::

[12]እነዚህን ሕግጋት ብታዳምጥና በጥንቃቄ ብትጠብቃቸው፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለአባቶችህ እንደ ማለላቸው ከአንተ ጋር የገባውን የፍቅር ኪዳኑን ይጠብቃል:: [13]ይወ ድሃል፤ ይባርክሃል፤ ያበዛሃልም:: ለአንተ ለማስጠት ለአባቶችህ በማለላቸው ምድር የማሕፀ ንህን ፍሬ፣ የምድርህን ሰብል:- እህልህን፣ አዲሱን ወይንና ዘይት፤ የከብት መንጋህን ጥጆች፣ የበግና የፍየል መንጋህን ግልገሎች

6፥21 ዘጸ4፥34
6፥24 ዘጸ10፥12፤ 30፥6፤መዝ27፥12፤ 41፥2፤86፥11፤ ኤር32፥39፤ሮሜ10፥5
6፥25 ዘጸ24፥13፤ መዝ103፥18፤119፥34፥ 55፤ሮሜ9፥31
7፥1 ዘፍ10፥16፡ 17፤13፥7፤15፥20፤ ዘሌ14፥34፤ዘጸ1፥7፤ 4፥38፤20፥16-18፤ 31፥3፤ኢሱ3፥10
7፥2 ቍ16፤ ዘፀ23፥32፤ዘኍ31፥17፤ ዘጸ2፥33፡34፤13፥8፤ 19፥13፤25፥12፤ 33፥27፤ኢሱ11፥11፤
7፥3 ዘፀ34፥15-16፤ ኢሱ22፥16፤ዳን9፥7
7፥4 ዘጸ4፥26፤ መሳ3፥6፤
7፥5 ዘፀ23፥24፤ 34፥13ዘጸ16፥21፤
7፥6 ዘፍ17፥7፤ ዘፀ8፥22፤19፥6፤34፥9፤ ዘሌ27፥30፤ዘጸ14፥2፤ 26፥19፤1ነገ3፥8፤ መዝ30፥4፤37፥28፤ 50፥5፤52፥9፤ ኢሳ41፥9፤43፥1፤ ሕዝ20፥5፤ሮሜ9፥4፤ ቲቶ2፥14
7፥7 ዘፍ22፥17፤ 34፥30፤ ዘጸ4፥37፤ 10፥22
7፥8 ዘፀ3፥20፤6፥6፤ 13፥14፤32፥13፤ ዘኍ14፥8፤ዘጸ4፥37፤ 1ነገ10፥9፤2ዜና2፥11፤ መዝ44፥3፤ሮሜ11፥28፤
7፥9 ቍ12፤ ዘፀ20፥6፤ዘጸ4፥35፤ 5፥10፤1ነገ8፥23፤ 2ዜና6፥14፤ነህ1፥5፤ 9፥32፤መዝ18፥25፤ 33፥4፤108፥4፤ 145፥13፤146፥6፤ ኢሳ49፥7፤ኤር42፥5፤ ሆሴ11፥12፤1ቆሮ1፥9
7፥10 ዘሌ26፥28፤ ዘኍ10፥35፤ናሆ1፥2
7፥12 ዘሌ26፥3-13፤ ዘጸ28፥1-14፤ መዝ105፥8-9፤ ሚክ7፥20
7፥13 ዘፍ17፥6፤ 27፥28፤49፥25፤ዘፀ1፥7፤ዘጸ1፥10፤13፥17፤28፥4፤ 30፥5፤ዘኍ18፥12፤ መዝ11፥5፤107፥38፤146፥8፤ምሳ15፥9፤ ኢሳ51፥1፤ዮሐ14፥21

[1]2 በዚህና በቍጥር 26 ላይ የዕብራይስጡ ቃል አንድን ነገር ወይም አንድን ሰው ሙሉ በሙሉ በማጥፋት ለእግዚአብሔር መስጠትን የሚያሳይ ነው::
[5]5 በዚህ መጽሐፍም ሆነ በሌላ ስፍራ ይህ የአሼራን ምስል ዐምድ የሚያመለክት ነው::

6፥23 *ሊያስገባን ... አወጣን፤* የዘፀ 6፥7-8 ማብ ይመ::

6፥25 *ጽድቃችን፤* እዚህ ላይ ምናልባት ራሱን በሕዝቡ የዕለት ትዕለት ሕይወት ውስጥ ከገለጠውና የቃል ኪዳን አምላክ ከሆነው ከእግዚአብሔር ጋር ያለውን እውነተኛ ግንኙነት ይገልጻል (24፥13 ይመ)::

7፥1 *ኬጢያውያን ... ኢያቡሳውያን፤* 20፥17 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 10፥6፡ 15-18፤ 13፥7 ማብ ይመ:: *ሰባቱን አሕዛብ፤* የዘጸ 3፥8 ማብ ይመ::

7፥2-5 *ከእነርሱ ጋር አትዋዋል፤ ... ከእነርሱም ጋር ጋብቻ አታድርግ፤ መሠዊያዎቻቸውን አፈራርሱ፤* እስራኤል ከከነዓን ጣዖት አምላኪ ሕዝቦች ጋር ምንም ዐይነት ፓለቲካዊ፣ ማኅበራዊና ሃይማኖታዊ ግንኙነት መፍጠር የለባትም (ቍ 16፤ እንዲሁም የ2፥34 ማብ ይመ)::

7፥2 *ሁሉንም መደምሰስ አለብህ፤* የ2፥34 ማብ ይመ::

7፥4 *ሌሎችን አማልክት እንዲያመልኩ ስለሚያደርጉ፤* እግዚአብሔር እስራኤላውያንን ከሌሎች የውጭ ሕዝቦች ጋር ምንም ዐይነት ጋብቻ እንዳይፈጽሙ የከለከለው፣ በዘር ወይም በጐሣ ላይ በተመሠረተ ዐላማ ሳይሆን፣ ሕዝቡን ከመንፈሳዊ ብክለትና ክህደት ለመከላከል ሲል ነው (ለምሳሌ 1ነገ 11፥1-11፤ ነህ 13፥25-27 ይመ)::

7፥5 *መሠዊያዎቻቸውን ... የማምለኪያ ዐምዶቻቸውን ... የአሼራ ምስል ዐምዶቻቸውን፤* የከነዓን ሰዎች ለጣዖት አምልኮ የሚጠቀሙባቸው ነገሮች ናቸው (12፥3፤ 16፥21-22 ይመ)፤ በተጨማሪ የዘፀ 34፥13 ማብ ይመ::

7፥6 *ቅዱስ፤* ሊያረክሱ ከሚችሉ ሰዎች ወይም ማናቸውም ነገሮች ተለይቶ ለእግዚአብሔር ሙሉ በሙሉ የተሰጠ ማለት ነው (የዘፀ 3፥5 ማብ ይመ)::

7፥8 *እግዚአብሔር እናንተን ስለወደዳችሁ፤* "የፍቅር ቃል ኪዳኑ" (ቍ 9:12) የመነጨው እግዚአብሔር ለሕዝቡ ካለው ፍቅር የተነሣ ሲሆን፣ የተመሠረተው ደግሞ በእግዚአብሔር ባሕርይ ላይ ሆኖ በኪዳኑ የታቀፈ ነው:: እግዚአብሔር ሕዝቡን የወደደው በቍጥር ብዙ ወይም በአካሄዳቸው ንጹሕ ስለሆኑ አይደለም:: ይልቁን እርሱ እንዲያው የወደደው ሕዝቡ፣ ለእግዚአብሔር ፍቅር ምላሽ መስጠትና ከልብ መውደድ ይጠበቅበታል (ቍ 9-10፤ 9፥4-6 ይመ፤ እንዲሁም የ6፥5 ማብ ይመ)::

7፥9 *እግዚአብሔር ... አምላክ መሆኑን ዕወቅ፤* መዝ 100፥3 ይመ:: *ለሚወዱት ... እስከ ሺህ ትውልድ፤* የዘፀ 20፥6 ማብ ይመ::

7፥13 *እህልህን፣ አዲሱን ወይንና ዘይት፤* በብሉይ ኪዳን ውስጥ ይህ ሐረግ የዕርሻን፣ የወይንንና የወይራ ዘይትን ምርት በአጭሩ የሚገልጽ የተለመደ አባባል ነው (ለምሳሌ 11፥14፤

ይባርካል:: [14]ከሕዝቦች ሁሉ የበለጠ አንተ ትባረካለህ፤ ከአንተ ወይም ከከብቶችህ መካከል የማይወልድ ወንድ ወይም ሴት አይኖርም:: [15]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከማናቸውንም በሽታ ነጻ ያደርግሃል፤ በግብፅ የምታውቃቸውን እነዚያን አሠቃቂ በሽታዎች በሚጠሉህ ሁሉ ላይ እንጂ፣ በአንተ ላይ አያመጣብህም:: [16]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጅህ አሳልፎ የሚሰጥህን ሕዝቦች ሁሉ ማጥፋት አለብህ፤ አትዘንላቸው፤ ወጥመድ ስለሚሆኑብህም አማልክታቸውን አታምልክ::

[17]"እነዚህ አሕዛብ ከእኛ ይልቅ ጠንካሮች ስለ ሆኑ፣ እንዴት አድርገን እናስወጣቸዋለን?" ብለህ በልብህ ታስብ ይሆናል:: [18]ነገር ግን አትፍራቸው፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በፈርዖንና በግብፅ ሁሉ ላይ ያደረገውን በሚገባ አስታውስ:: [19]*ታላላቅ ፈተናዎችን*፣ *ታምራዊ ምልክቶችንና ድንቅ ነገሮችን አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አንተን ያወጣበትን ብርቱ እጅና የተዘረጋች ክንድ በገዛ ዐይንህ አይተሃል:: *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አሁን በምትፈራቸው ሕዝቦች ሁሉ ላይ ያንኑ ያደርጋል:: [20]ይልቁንም *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሕይወት ተርፈው፣ ከአንተ የተደበቁት እንኳ እስኪጠፉ ድረስ በመካከላቸው ተርብ ይሰድባቸዋል:: [21]በመካከልህ ያለው *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ታላቅና የሚያስፈራ አምላክ (ኤሎሂም) ስለ ሆነ አያስደንግጡህ:: [22]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እነዚህን ሕዝቦች ጥቂት በጥቂት ከፊትህ ያስወጣቸዋል፤ የዱር አራዊቱ ቍጥር በአካባቢህ እንዳይበራከት ሁሉንም በአንድ ጊዜ ማጥፋት አይፈቀድልህም፤ [23]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ግን እስኪጠፉ ድረስ ከባድ ትርምስ ፈጥሮባቸው በእጅህ አሳልፎ ይሰጥሃል:: [24]*ነገሥታታቸውን* በእጅህ ይጥላቸዋል፤ ስማቸውንም ከሰማይ በታች ታጠፋለህ:: እስክ ትደመስሳቸው ድረስ፣ አንተን መቋቋም የሚችል አንድም ሰው የለም:: [25]የአማልክታቸውን ምስሎች በእሳት አቃጥል፤ በላያቸው የሚገኘውን ብርና ወርቅ አትመኝ፤ ለራስህ አታድርግ፤ አለበለዚያ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ዘንድ አስጸያፊ ስለ ሆነ፣ ያሰናክልሃል:: [26]አስጸያፊ ነገርን ወደ ቤትህ ወይም ወደ ራስህ አታምጣ፤ አለበለዚያ አንተም እንደ እርሱ ለጥፋት ትዳረጋለህ፤ ፈጽመህ ጥላው፤ ተጸየፈውም፤ ለጥፋት የተለየ ነውና::

7፥14 ዘፀ23፥26
7፥15 ዘፀ9፥9፤ 15፥26፤23፥25፤ ዘዳ30፥8-10
7፥16 ቍ2፥24፤ ቍ25፤ዘፀ10፥7፤ ኢያ6፥2፤10፥26፤ መሳ3፥6፤ዕዝ9፥1፤ መዝ106፥36፤
7፥17 ዘኍ33፥53
7፥18 ዘኍ14፥9፤ ዘዳ1፥21፡29፤ መዝ105፥5፤119፥52
7፥19 ዘዳ4፥34፤ መዝ136፥12፤
7፥20 ዘፀ23፥28
7፥21 ዘፍ17፥7፤ ዳን10፥17፤ ኢያ3፥10፤ነህ1፥5፤ 9፥32፤መዝ47፥2፤ 66፥3፤68፥35፤ ኢሳ9፥6፤ዳን9፥4
7፥22 ዘፀ23፥28-30
7፥23 ዘፀ23፥27፤ ኢያ10፥10
7፥24 ቍ16፤ ዘፀ23፥31፤ዘዳ11፥25፤ ኢያ1፥5፤10፥8፡24፤ 21፥44፤23፥9፤ መዝ110፥5
7፥25 ቍ16፤ ዘፀ4፥14፤20፥17፤ 32፥20፤ዘዳ17፥1፤ ኢያ7፥21፤
7፥26 ዘሌ27፥28-29
8፥1 ዘፀ19፥5፤ ዘዳ4፥1፤ኢዩ36፥11፤ መዝ16፥11፤ሕዝ20፥19
8፥2 ዘፍ22፥1፤ ዘዳ29፥5፤መዝ136፥16፤ አሞ2፥10፤
8፥3 ቍ9፤ ዘፍ3፥19፤ ዘፀ16፥2-3፡4፤ 1ነገ8፥36፤2ዜና6፥27 36፥12፤ ኢዮ22፥22፤23፥12፤ መዝ25፥5፤44፥9፤ 94፥12፤104፥15፤ 119፥13፡171፤ 138፥4፤ምሳ18፥12፤ 28፥21፤ኢሳ2፥11፤ 51፥14፤ኤር42፥14፤ 44፥10፤ማቴ4፥4፤ ሉቃ4፥4
8፥4 ዘዳ29፥5፤ ነህ9፥21
8፥5 ዘዳ4፥36፤2 ሳሙ7፥14፤ኢዮ5፥17፤ 33፥19፥ምሳ3፥11-12፤ ዕብ12፥5-11፤ ራእ3፥19
8፥6 ዘፀ33፥13፤ዘዳ5፥33፤1ነገ3፥14፤ መዝ81፥13፤95፥10
8፥7 ዘዳ11፥9-12፤መዝ106፥24፤ ኤር2፥7፤ 3፥19፤ሕዝ20፥6፤
8፥8 ዘፍ49፥11፤ዘፀ9፥31፤ዘኍ13፥23፤ዘዳ32፥13፤ 1ነገ4፥25፤ መዝ81፥16
8፥9 ቍ31 መሳ18፥10፤ኢዮ28፥2
8፥10 ዘዳ6፥10-12

## *እግዚአብሔርን አትርሳ*

**8** በሕይወት እንድትኖሩ፣ እንድትበዙና *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለአባቶቻችሁ በመሐላ ተስፋ የገባላቸውን ምድር ገብታችሁ እንድትወርሱ፣ ዛሬ እኔ የምሰጥህን እያንዳንዱን ትእዛዝ ለመከተል ጥንቃቄ አድርጉ:: [2]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዞቹን መጠበቅህንና በልብህ ያለውን ለማወቅ፣ ትሑት ሊያደርግህና ሊፈትንህ በእነዚህ አርባ ዓመታት በዚህ ምድረ በዳ ጕዞህ ሁሉ እንዴት እንደመራህ አስታውስ:: [3]ሰው *ከእግዚአብሔር* (ያህዌ) አፍ በሚወጣው በእያንዳንዱ ቃል እንጂ፣ በእንጀራ ብቻ እንደማይኖር ሊያስተምርህ አስራበህ፤ አንተም ሆንህ አባቶችህ የማታውቁትን መና መገበህ፤ [4]በእነዚህ አርባ ዓመታት ውስጥ ልብስህ አላለቀም፤ እግርህም አላበጠም:: [5]ስለዚህ ሰው ልጁን እንደሚቀጣ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔርም (ያህዌ ኤሎሂም) አንተን እንደሚቀጣህ በልብህ ዕወቅ::

[6]በመንገዶቹ በመሄድና እርሱንም በማክበር፣ *የአምላክህን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዞች ጠብቅ:: [7]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ጅረቶችና የኵሬ ውሃ ወዳለበት፣ ምንጮች ከየሸለቆውና ከየኰረብታው ወደሚፈሱበት ወደ መልካሚቱ ምድር ያገባሃልና ነው፤ [8]ስንዴና ገብስ፣ ወይንና የበለስ ዛፎች፣ ሮማን፣ የወይራ ዘይትና ማር የሚገኝባት ምድር፤ [9]ምንም ነገር የማይታጣባት፣ የዳቦም ዕጦት የሌለባት፣ ዐለቶች ብረት የሆኑባት፣ ከኰረብቶቿም መዳብ ቈፍረህ ልታወጣ የምትችልባት ምድር ናት::

[10]በልተህ በምትጠግብበት ጊዜ እንዲህ ያለች መልካም ምድር ስለ ሰጠህ *አምላክህን* እግዚአብ

---

14፥23፤ 18፥4፤ 28፥51 *ይመ*)::

7፥15 *በሽታዎች ... በአንተ ላይ አያመጣብህም፤* የ28፥60 *ማብ ይመ*::

*7፥16፤* የኢያሱን መጽሐፍ መግቢያ *ይመ*::

7፥18 *አስታውስ፤* የ4፥10 *ማብ ይመ*::

7፥20 *ተርብ፤* የዘፀ 23፥28 *ማብ ይመ*::

7፥22 *እግዚአብሔር ... ያስወጣቸዋል፤* የ3፥22 *ማብ ይመ*::

*7፥25-26፤* የአካንን ታሪክ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (ኢያ 6፥17-19፤ 7፥1፡ 20-25)::

7፥26 *ለጥፋት ትዳረጋለህ፤* የ2፥34 *ማብ ይመ*::

8፥2 *ሊፈትንህ፤* ቍ 16 *ይመ*፤ በተጨማሪም የዘፍ 22፥1 *ማብ ይመ*:: *አስታውስ፤* የ4፥10 *ማብ ይመ*::

8፥3 *ሰው ... በእንጀራ ብቻ እንደማይኖር፤* የ6፥13 *ማብ ይመ*፤ ኢየሱስ በዲያብሎስ በተፈተነ ጊዜ ይህን ቃል ጠቅሶአል (ማቴ 4፥4፤ ሉቃ 4፥4 *ይመ*):: እንጀራ ሕይወትን ይደግፋል እንጂ የሕይወት ዋስትና አያሆንም፤ ሕይወት የእግዚአብሔርን ቃል ማለትም ትእዛዙንና ተስፋውን (ቍ 1፡18 *ይመ*) ለሚያምኑና ለሚጠብቁ ከእግዚአብሔር ዘንድ የምትሰጥ ናት:: እግዚአብሔር ሕዝቡን ወደ ምድረ በዳ ወስዶ እየጕዳ በማሠልጠን (ቍ 5) ይህንን መሠረታዊ እውነት አስተማራቸው:: በዚያም እግዚአብሔርን ብቻ ሙሉ በሙሉ እስኪታመኑ ድረስ ትሑት ተደርገዋል (ቍ14 ጋር ያነጻጽሩ)፤ *መና* ቍ 16 *ይመ*፤ እንዲሁም የዘኍ 11፥7 *ማብ ይመ*::

*8፥7-9፤* እስራኤላውያን ገብተው ሊወርሷት የተቃረቡትንና በተፈጥሮ ሀብቷና በለምነቷ እጅግ የታወቀችውን የተስፋይቱን ምድር የሚገልጽ ክፍል ነው (11፥8-12 *ይመ*)::

8፥9 *ብረት ... መዳብ፤* የደቡብ ሊባኖስ ተራሮችና ከገሊላ ባሕር በስተ ምሥራቅ እንዲሁም ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ የሚገኘው ክፍል የብረት ማዕድን ይገኝበታል:: ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ የሚገኘው የዓረባ ምድር የመዳብና የብረት ሀብት እጅግ የሞላበት ስፍራ ነው:: በዚህ ስፍራ የነበረው አንዳንድ የመዳብ ማዕድን ቁፋሮ ከንጉሥ ሰሎሞን ዘመንና ከዚያም በፊት ጀምሮ የታወቀ ነው:: በሰሎሞን ዘመን፣ ደርታን የናስ ሥራ ማእከል ነበረች (1ነገ 7፥45-46):: ከዚህ ስፍራ በቍፋሮ የተገኙ አንዳንድ የናስ ዕቃዎች ከንጉሥ ሰሎሞን ዘመን በፊት እንደ ነበሩ ታውቆአል፤ በአሁኑ ጊዜ በኔጌብ አካባቢ ቲምናህ በተባለ ቦታ የመዳብ ቍፋሮ ሥራ እየተከናወነ ነው::

ሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ባርከው። [11]በዛሬዪቱ ዕለት የምሰጥህን ትእዛዙን፣ ሕጉንና ሥርዐቱን ባለመጠበቅ *አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) እንዳትረሳው ተጠንቀቅ። [12]አለበለዚያ በልተህ ስትጠግብና ጥሩ ጥሩ ቤቶችን ሠርተህ መኖር ስትጀምር፣ [13]ደግሞም የከብት፣ የበግና የፍየል መንጋህ ሲበዛ፣ ብርህና ወርቅህ ሲበረክት፣ ያለህም ሁሉ በላይ በላዩ እየጨመረ ሲሄድ፣ [14]ልብህ ይታበይና ከባርነት ምድር፣ ከግብፅ *ያወጣህን አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትረሳለህ። [15]በዚያ ጭልጥ ባለና አስፈሪ ምድረ በዳ፣ በዚያ በሚያስጠማና ውሃ በማይገኝበት ደረቅ መሬት፣ መርዘኛ እባብና ጊንጥ ባለበት ምድረ በዳ መራህ፤ ከጽኑ ዐለትም ውሃ አፈለቀልህ። [16]በመጨረሻ መልካም እንዲሆንልህ፣ አንተን ትሑት ለማድረግና ለመፈተን፣ አባቶችህ ፈጽሞ የማያውቁትን መና በምድረ በዳ መገበህ። [17]ምናልባትም፣ "ይህን ሀብት ያፈራሁት በጕልበቴና በእጄ ብርታት ነው" ብለህ በልብህ *ታስብ* ይሆናል። [18]ነገር ግን ሀብት እንድታፈራ ችሎታ የሰጠህ፣ ለአባቶችህም በመሐላ የገባውን ኪዳን ያጸናልህ እርሱ ስለ ሆነ፣ *አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) አስበው።

[19]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ብትረሳና ሌሎችን አማልክት ብትከተል፣ ብታመልክና ለእነርሱ ብትሰግድላቸው በእርግጥ እንደምትጠፋ ዛሬ እመሰክርባችኋለሁ። [20]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከፊታችሁ ያሉትን አሕዛብ እንዳጠፋቸው ሁሉ፣ *ለአምላካችሁ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባለመታዘዛችሁ እናንተም ትጠፋላችሁ።

## የሕዝቡ አለመታዘዝ

**9** እስራኤል ሆይ፣ ስማ፤ ሰማይ ጠቀስ ቅጥር ያላቸው ታላላቅ ከተሞች ያሏቸውን፣ ከአንተ ይልቅ ታላቅና ብርቱ፣ የሆኑትን አሕዛብ አስለቅቀህ ለመግባት ዮርዳኖስን አሁን ትሻገራለህ። [2]ዔናቃውያን ብርቱና ቁመተ ረጃጅም ሕዝቦች ናቸው፤ ስለ እነርሱ ታውቃለህ፤ "ዔናቃውያንን ማን ሊቋቋማቸው ይችላል?" ሲባልም ሰምተሃል። [3]ይሁን እንጂ እንደሚባላ እሳት ከፊትህ ቀድሞ የሚሻገረው *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) መሆኑን ዛሬ እርግጠኛ ሁን፤ እነርሱን ያጠፋቸዋል፤ በፊትህም ድል ያደርጋቸዋል፤ አንተም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሰጠህ ተስፋ መሠረት ታስወጣቸዋለህ፤ በፍጥነትም ትደመስሳቸዋለህ።

[4]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እነርሱን ከፊትህ ካስወጣቸው በኋላ፣ "ይህችን ምድር እንድወርስ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ወደዚህ ያመጣኝ፣ ከጽድቄ የተነሣ ነው" ብለህ በልብህ አታስብ። በዚህ አይደለም፤ እነዚህን አሕዛብ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከፊትህ የሚያሳድዳቸው በክፋታቸው ምክንያት ነው። [5]ምድራቸውን ገብተህ የምትወርሳት ከጽድቅህ ወይም ከልብህ ቅንነት የተነሣ ሳይሆን፣ ለአባቶችህ ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ የማለላቸውን ቃል ለመፈጸም *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እነዚህን አሕዛብ ከክፋታቸው የተነሣ ከፊትህ ስለሚያባርራቸው ነው። [6]ስለዚህ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ይህችን መልካም ምድር እንድትወርሳት የሚሰጥህ ከጽድቅህ የተነሣ አለመሆኑን አስተውል፤ አንተ ዐንገተ ደንዳና ነህና።

## የወርቁ ጥጃ

[7]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) በምድረ በዳ እንዴት እንዳስቈጣኸው አስታውስ፤ ከቶም አትርሳ። ከግብፅ ከወጣህበት ዕለት አንሥቶ እዚህ ቦታ እስከ ደረስህበት ጊዜ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ላይ እንዳመፅህ ነህ። [8]በኮሬብ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) ለቍጣ አነሣሣችሁት፤ እርሱም እናንተን ሊያጠፋችሁ እጅግ ተቈጣ። [9]እኔም የድንጋይ ጽላቶቹን፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከእናንተ ጋር የገባውን የኪዳን ጽላቶች ለመቀበል ወደ ተራራው በወጣሁ ጊዜ፣ እህል ሳልበላ፣ ውሃም ሳልጠጣ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ቈየሁ፤ [10]*በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ጣት የተጻፈባቸውን ሁለት የድንጋይ ጽላቶች *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሰጠኝ፤ በተከበባች ሁበት ዕለት *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከተራራው ላይ፣ በእሳት ውስጥ ሆኖ ለእናንተ የነገራችሁ ትእዛዛት ሁሉ በእነርሱ ላይ ነበሩባቸው።

[11]አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ከተፈጸመ በኋላ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሁለቱን የድንጋይ ጽላቶች ማለትም የኪዳኑን ጽላቶች ሰጠኝ። [12]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ)፣ "ተነሥ፤ ከግብፅ ያወጣሃቸው ሕዝብህ ረክሰዋልና ፈጥነህ ከዚህ ውረድ፤ እኔ ካዘዝኋቸው ፈጥነው ፈቀቅ ብለዋል፤ ቀልጦ የተሠራ ጣዖትም ለራሳቸው አበጅተዋል" ብሎ ነገረኝ።

[13]ደግሞም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዲህ አለኝ፤ "ይህን ሕዝብ አይቼዋለሁ፤ በእርግጥ ዐንገተ

8፥11 ዘዳ4፥9
8፥12 ምሳ30፥9፤ ሆሴ13፥6
8፥14 ቍ11፤ መዝ78፥7፤106፥21
8፥15 ዘፀ17፥6፤ ዘኍ21፥6፤ ዘዳ1፥19፤ 32፥10፤32፥13፤ ኢዮ28፥9፤ መዝ78፥15፤ 114፥8፤ ኢሳ14፥29፤ 30፥6፤
8፥16 ዘፍ22፥1፤ ዘፀ16፥14፡15
8፥17 ዘዳ9፥4፡7፡ 24፤31፥27፤ መሳ7፥2፤ መዝ44፥3፤ ኢሳ10፥13
8፥18 ዘፍ26፥13፤ ዘዳ26፥10፤28፥4፤ 1ሳሙ2፥7፤ መዝ125፥13፤ 112፥3፤ ምሳ8፥18፤ 10፥22፤ መክ9፥11፤ ሆሴ2፥8፤
8፥19 ዘዳ6፥14፤ ዘዳ4፥26፤30፥18፤ መዝ16፥4፤ ኤር7፥6፤ 13፥10፤25፥6
8፥20 2ነገ21፥2፤ መዝ10፥16፤ ሕዝ5፥5-17
9፥1 ዘፍ11፥4፤ ዘኍ13፥28፤35፥10፤ ዘዳ4፥38፤
9፥2 ዘኍ13፥22፤ ኢሱ11፥22
9፥3 ዘፀ15፥7፤ 19፥18፤23፥31፤ ዘዳ31፥3፤ ኢሱ3፥11፤ ዕብ12፥29
9፥4 ዘፀ23፥24፤ ዘዳ8፥17፤18፥9-14፤ ዘሌ18፥21፡24-30፤ 2ነገ16፥3፤17፥8፤ 21፥2፤ ዕዝ9፥11፤
9፥5 ዘፍ12፥7፤ ዘዳ4፥38፤11፥23፤ ዘዳ18፥9፤ ዘሌ18፥25፤ ሕዝ36፥32፤ ኤፌ2፥9
9፥6 ዘፀ32፥9፤ ሐሥ7፥51
9፥7 ዘኍ11፥33፤ ዘፀ14፥11፤23፥21
9፥8 ዘፀ32፥7-10፤ ዘኍ16፥46፤ 1ሳሙ28፥18፤ ዕዝ9፥14፤ ኢዮ20፥28፤ መዝ2፥12፤7፥11፤ 69፥24፤110፥5፤ ኢሳ9፥19፤ ሕዝ20፥13፤
9፥9 ዘፍ7፥4፤ ዘፀ24፥12፤ ዘዳ4፥13፤
9፥10 ዘፀ31፥18፤ ዘዳ10፥4፤18፥16
9፥11 ዘፍ7፥4፤ ዘፀ24፥12
9፥12 ዘዳ4፥16፤ መሳ2፥17
9፥13 ቍ6፤ ዘዳ10፥16

8፥11፡14፡19 *እንዳትረሳ ... ትረሳለህ ... ብትረሳ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

8፥15 *ከጽኑ ዐለትም ውሃ፤* ዘፀ 17፥6 እና ማብ ይመ።

8፥16 *ለመፈተን፤* ቍ 2 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 22፥1 ማብ ይመ።

*8፥17-18፤* ዘካ 4፥6 እና ማብ ይመ።

8፥18 *አስበው፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

9፥1 *እስራኤል ሆይ፤ ስማ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

9፥2 *ዔናቃውያን፤* የ1፥28 ማብ ይመ።

9፥3 *እንደሚባላ እሳት፤* 4፥24 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 24፥17 ማብ ይመ። *በፊትህም ድል ያደርጋቸዋል፤ አንተም ... ታስወጣቸዋለህ፤* እግዚአብሔር በእስራኤላውያን ፊት መሄድ ብቻ ሳይሆን፣ ድልን ሊሰጣቸው ኀይሉን በእነርሱ ውስጥ ገልጦአል። የእስራኤል ሕዝብ ለጦርነት በወጣበት ጊዜ ሁሉ ከእስራኤል ሰራዊት ጋር በመሆን እግዚአብሔር ለእስራኤል ይዋጋ እንደነበር በዘዳግም መጽሐፍና በታሪክ መጻሕፍት ውስጥ ተጠቅሶአል።

9፥4 *ከጽድቄ የተነሣ፤* የ7፥8 ማብ ይመ። *እነዚህን አሕዛብ ... በክፋታቸው ምክንያት፤* የዘፍ 15፥16 ማብ ይመ።

9፥6፡13 *ዐንገተ ደንዳና፤* 10፥16፤31፥27 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 32፥9 ማብ ይመ።

9፥7፡27 *አስታውሱ ... አትርሳ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

9፥9 *የድንጋይ ጽላቶቹን የኪዳን ጽላቶች፤* የዘፀ 20፥1፤ 34፥38 ማብ ይመ።

9፥10 *በእርሱ ጣት፤* የዘፀ 8፥19 ማብ ይመ። *ሁለት የድንጋይ ጽላቶች፤* የዘፀ 31፥18 ማብ ይመ።

ደንዳና ሕዝብ ነው፤ [14]አጠፋቸውና ስማ ቸውንም ከሰማይ በታች እደመስሰው ዘንድ ተወኝ፤ አንተንም ከእነርሱ ይልቅ ብርቱና ብዙ ሕዝብ አደርግሃለሁ።”

[15]ስለዚህ ተራራው በእሳት እየተቀጣጠለ ሳለ፣ ሁለቱን የቃል ኪዳን ጽላቶች በሁለቱም እጆቼ እንደያዝሁ[ሀ] ከተራራው ተመልሼ ወረድሁ። [16]በእርግጥ *በአምላካችሁ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ላይ ኀጢአት *ሠርታችሁ* እንደ ነበር ተመለከትሁ፤ ቀልጦ የተሠራ የጥጃ ምስልም ለራሳችሁ አበጃችሁ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እናንተን ካዘዛችሁ መንገድ በፍጥነት ወጥታችሁ ነበር። [17]ስለዚህ ሁለቱን ጽላቶች ወስጄ ከእጆቼ አሽቀንጥሬ በፊታችሁ ሰባበርኋቸው።

[18]ከዚያም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ክፉ ነገርን በመፈጸም ለቍጣ እንዲነሣሣ የሚያደርገውን ኀጢአት ሁሉ ስለ ሠራችሁ፣ እህል ውሃ ሳልቀምስ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት እንደ ገና *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት በግምባሬ ተደፋሁ። [19]እናንተን ሊያጠፋችሁ ክፉኛ ተቈጥቶ ነበርና፣ እኔም *የእግዚአብሔርን* (የያህዌ) ቍጣና መዓት ፈራሁ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ግን እንደ ገና ሰማኝ። [20]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) አሮንን ሊያጠፋው ክፉኛ ተቈጥቶ ነበር፤ በዚያን ጊዜ ለአሮንም ጸለይሁ። [21]ደግሞም ያን የኀጢአት *ሥራችሁን*፣ አበጅታችሁት የነበረውን ጥጃ ወስጄ፣ በእሳት አቃጠልሁት፤ ከዚያም ሰባብሬ እንደ ትቢያ ዱቄት እስኪሆን ድረስ ፈጭቼ ከተራራው በሚወርደው ጅረት ውስጥ በተንሁት።

[22]በተቤራም፣ በማሳህና በቂብሮት ሐታአዋ *እግዚአብሔርን* (ያህዌ) አስቈጣሁት።

[23]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከቃዴስ በርኔ ባስወጣችሁ ጊዜ፣ “ውጡ፤ የሰጠኋችሁንም ምድር፣ ርስት አድርጋችሁ ውረሷት” አላችሁ። እናንተ ግን *በአምላካችሁ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዝ ላይ ዐመፃችሁ፤ እርሱን አልታመናችሁበትም፤ አልታዘዛችሁትምም። [24]እኔ እናንተን ካወቅኋችሁ ጊዜ ጀምሮ፣ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ላይ እንዳመፃችሁ ናችሁ።

[25]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እናንተን እንደሚያጠፋችሁ ተናግሮ ስለ ነበር፣ በእነዚያ አርባ ቀናትና አርባ ሌሊቶች በእግዚአብሔር ፊት በግንባሬ ተደፋሁ፤ [26]እንዲህም በማለት ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጸለይሁ፤ “ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ (አዶናይ ያህዌ) በታላቅ ኀይልህ የተቤዠኸውንና በኀያል ክንድህ ከግብፅ ያወጣኸውን፣ *ያንተ* ርስት የሆነውን ሕዝብህን አታጥፋ።

9፥14 ዘፀ32፥10፤ ዘኍ14፥12፤ ኤር7፥16
9፥15 ዘፀ32፥15
9፥16 ዘፀ32፥4
9፥18 ቍ9፤ ዘፀ32፥31፤ ዘዳ34፥28
9፥19 ቍ26፤ ዘፀ32፥14፤34፥10፤ ዘኍ11፥2፤1ሳሙ7፥9፤ ኤር15፥1፤ዕብ12፥21፤
9፥21 ዘፀ32፥20፤ መዝ18፥42፤ ኢሳ2፥18፤29፥5፤ 40፥12፤ሚክ1፥7
9፥22 ዘፀ17፥7፤ ዘኍ1፥53፤11፥3፡34፤
9፥23 ዘኍ14፥9፤ ዘዳ1፥2፡21፡32፤ መዝ106፥24
9፥24 ዘዳ8፥17
9፥25 ቍ18፤ ዘፍ7፥4፤ዘፀ33፥17
9፥26 ቍ19፤ ዘፀ6፥6፤32፥11፤ 33፥13፤34፥9፤ ዘዳ15፥15፤2ሳሙ7፥23፤ መዝ78፥35
9፥27 ቍ6፤ ዘፀ32፥9
9፥28 ዘፀ32፥12፤ ዘዳ1፥27፤32፥27፤ ኢሱ7፥9
9፥29 ዘፀ33፥13፤ 34፥9፤ዘዳ4፥34፤32፥9፤ ነህ1፥10፤ኤር27፥5፤ 32፥17
10፥1 ዘፀ34፥1-2
10፥2 ዘፀ25፥16፡ 21፤2ዜና5፥10፤6፥11
10፥3 ዘፀ34፥4፤ 37፥1-9
10፥4 ዘፀ24፥12፤ 34፥28፤20፥1፤ዘዳ9፥10
10፥5 ዘፀ19፥11፤ 25፥10፡21፤ 1ሳሙ3፥3፤1ነገ8፥9
10፥6 ዘፀ6፥23፤ ዘኍ20፥20-28፤ 27፥13፤33፥30
10፥7 ዘኍ33፥32-34፤መዝ42፥1፤ መኃ5፥12፤ኢሳ32፥2
10፥8 ዘፍ48፥20፤ ዘኍ3፥6፤10፥33፤ 16፥9፤1ዜና23፥26
10፥9 ዘኍ18፥20

[27]ባሪያዎችህን አብርሃምን፣ ይስሐቅንና ያዕቆብን አስብ፤ የዚህን ሕዝብ ልብ ደንዳናነት፣ ክፋትና ኀጢአት አትመልከት። [28]አለበለዚያ እኛንካመጣህበት ምድር ያሉ ሰዎች ‘*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ተስፋ ወደ ሰጣቸው ምድር ሊያገባቸው ስላልቻለና ስለጠላቸው፣ በምድረ በዳ ሊገድላቸው አወጣቸው ይላሉ።’ [29]ነገር ግን እነርሱ በታላቅ ኀይልህና በተዘረጋች ክንድህ ያወጣሃቸው ሕዝብህና ርስትህ ናቸው።”

## በድንጋሚ የተሰጡ የመጀመሪያዎቹ ዐይነት ጽላቶች

**10** በዚያን ጊዜ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንዲህ አለኝ፤ “እንደ *መጀመሪያዎቹ* ያሉ ሁለት የድንጋይ ጽላቶች ቀርጸህ ወደ እኔ ወደ ተራራው ላይ ውጣ፤ *ታቦትም* ከዕንጨት *ሥራ*። [2]እኔም አንተ በሰበርሃቸው በፊተኞቹ ጽላቶች ላይ የነበሩትን *ቃላት* በእነዚህኞቹ ጽላቶች ላይ እጽፋቸዋለሁ፤ አንተም በ*ታቦቱ* ውስጥ *ታኖራቸዋለህ*።”

[3]ስለዚህ ከግራር ዕንጨት *ታቦት* ሠራሁ፤ እንደ ፊተኞቹ ያሉ ሁለት የድንጋይ ጽላቶች ቀረጽሁ፤ ሁለቱንም ጽላቶች በእጆቼ ይዤ ወደ ተራራው ወጣሁ። [4]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በስብሰባው ቀን፣ በእሳት ውስጥ ሆኖ ለእናንተ የተናገራቸውንና ቀድሞ ጽፎአቸው የነበሩትን ዐሥሩን ትእዛዛት በእነዚህ ጻላቶች ላይ ጻፋቸው። *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) እነርሱን ለእኔ ሰጠኝ። [5]ከዚያም ከተራራው ተመልሼ ወረድሁ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ባዘዘኝ መሠረት በሠራሁት *ታቦትም* ውስጥ፣ ጽላቶቹን አስቀመጥኋቸው፤ አሁንም እዚያ ናቸው።

[6]እስራኤላውያን ከብኤሮት ብኔያዕቃን፣ የያዕቃን ልጆች ከቈፈሯቸው የውሃ ጕድጓዶች ተነሥተው ወደ ሞሴራ ተጓዙ፤ አሮንም በዚያ ቦታ ሞቶ ተቀበረ፤ ልጁ አልዓዛር በእርሱ ምትክ ካህን ሆነ። [7]ከዚያም ተነሥተው ጕድጎዳ ወደተባለ ስፍራ፣ ቀጥሎም የውሃ ፈሳሾች ወዳሉባት ዮጥባታ ወደምትባል ምድር ተጓዙ። [8]በዚያን ጊዜ፣ ዛሬም እንደሚያደርገው ያገለግል ዘንድ፣ *በእግዚአብሔርም* (ያህዌ) ፊት እንዲቆምና በስሙ እንዲባርክ *የእግዚአብሔርንም* (ያህዌ) የኪዳኑን ታቦት እንዲሸከም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሌዊን ነገድ ለየ። [9]ሌዋዊ በወንድሞቹ መካከል ድርሻም ሆነ ርስት የሌለው ከዚህ የተነሣ ነው፤ *አምላክህ*

[ሀ]15 ወይም፣ *ሁለቱም የቃል ኪዳን ጽላቶች ከእኔ ጋር ነበሩ፤ አንዱም በአንዱ፣ ሌላውም በሌላው እጄ ነበር* ተብሎ መተርጐም ይችላል።

9፥11-12፤ ዘፀ 31፥18-32፥20 ይመ።

9፥19 *እግዚአብሔር ግን እንደ ገና ሰማኝ፤* ሙሴ በዚህ ጊዜ ወደ እግዚአብሔር ያቀረበው የምልጃ ጸሎት (ቍ 26-29)፣ ለእስራኤል ሕዝብ ሕልውና ከተጸለዩት ታላላቅ ጸሎቶች አንዱ ነው (1ሳሙ 7፥5፡8-9፤ ኤር 15፥1 ይመ)።

9፥22 *ተቤራ፤* ዘኍ 11፥3 ይመ፤ “ተቤራ” ማለት “የሚነድ፣ የሚበራ” ማለት ነው። *ማሳህ፤* 6፥16፤ 33፥8፤ እንዲሁም የዘፀ 17፥7 ማብ ይመ። *ቂብሮት ሐታአዋ፤* ዘኍ 11፥34 ይመ፤ “ቂብሮት ሐታአዋ” ማለት “የምኞች መቃብር” ማለት ነው።

9፥23 *ቃዴስ በርኔ፤* የዘፍ 14፥7 ማብ ይመ።

9፥27 *አትመልከት፤* የሐሥ 17፥30 ማብ ይመ።

10፥1-3 *ታቦት፤* የዕብራይስጡ ቃል ትርጕሙ “ሣጥን” ማለት ነው።

10፥1 *ሁለት የድንጋይ ጽላቶች፤* የዘፀ 31፥18 ማብ ይመ።

10፥2 *በታቦቱ ውስጥ ታኖራቸዋለህ፤* የዘፀ 16፥34፤ 25፥16 ማብ ይመ።

*10፥3፤* ዘፀ 34-37 እንደሚያሳየውና በዚህ ቦታ እንደተጠቀሰው፣ የሁነቶቹ ቅደም ተከተል በዘፀአት መጽሐፍ ላይ ከተመለከተው የተለየ ነው።

*10፥6-9፤* በመኻል የገባ የታሪክ ዘገባ ሲሆን፣ ታሪኩ የተመ

እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በነገረው መሠረት ርስቱ እግዚአብሔር (ያህዌ) ነው::

[10]እኔም በመጀመሪያው ጊዜ እንዳደረግ ሁት፣ በተራራው ላይ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ቈየሁ፤ በዚህ ጊዜም እግዚአብሔር (ያህዌ) እንደ ገና ሰማኝ፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) አንተን ሊያጠፋ አልፈቀደም:: [11]ስለዚህም እግዚአብሔር (ያህዌ)፣ "ሂድ፤ ለአባቶቻቸው ለመስጠት ወደ ማልሁላቸው ምድር ገብተው እንዲወርሱ ሕዝቡን ምራ" አለኝ::

### እግዚአብሔርን (ያህዌ) ፍራ

[12]አሁንም እስራኤል ሆይ፤ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከአንተ የሚፈልገው ምንድን ነው? አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) እንድት ፈራው፣ በመንገዶቹ ሁሉ እንድትሄድ፣ እንድት ወደው፣ በፍጹም ልብህ፣ በፍጹም ነፍስህ እንድታገለግለው፣ [13]መልካም እንዲሆንልህና ዛሬ እኔ የምሰጥህን ትእዛዞችና ሥርዐቶች እን ድትጠብቅ አይደለምን?

[14]ሰማያት፣ ሰማየ ሰማያት፣ ምድርና በእ ርሷም ያለው ሁሉ የአምላክህ የእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ነው:: [15]ነገር ግን እግዚአብሔር (ያህዌ) አባቶችህን ስላፈቀረ፣ ወደዳቸው፤ ዛሬም እንደ ሆነው የእነርሱ ዘር የሆናችሁትን እናንተን ከአሕዛብ ሁሉ ለይቶ መረጣችሁ:: [16]ስለዚህ የልባችሁን ሸለፈት ግረዙት፤ ከእንግዲህም ወዲያ ዐንገተ ደንዳና አትሁኑ:: [17]አምላካችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የአማልክት አምላክ (ኤሎሂም)፣ የጌቶች ጌታ (አዶናይ)፣ ታላቅ አምላክ (ኤሎሂም)፣ ኀያልና የሚያስፈራ፣ አድልዎ የማያደርግ፣ መማለጃም የማይቀበል ነውና:: [18]እርሱ አባት ለሌላቸውና ለመበለቶች ይፈርዳል፤ መጻተኛውንም ምግብና ልብስ በመስጠት ይወዳል:: [19]ስለዚህ እናንተም በግብፅ ምድር መጻተኞች ነበራችሁና መጻተኛን ውደዱ:: [20]አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ፍራ፤ አምልከውም፤ ከእርሱም ጋር ተጣበቅ፤ በስሙም ማል:: [21]እርሱ ውዳሴህ ነው፤ በገዛ ዐይኖችህ ያየሃቸውን፣ እነዚያን ታላላቅና አስፈሪ ነገሮች ያደረገልህ አምላክህ (ኤሎሂም) ነው:: [22]አባቶችህ ወደ ግብፅ ሲወርዱ ሰባ ነበሩ፤ አሁን ግን አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንደ ሰማይ ከዋክብት አብዝቶሃል::

### እግዚአብሔርን (ያህዌን) ውደድ፤ ታዘዘውም

# 11

እንግዲህ አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ውደድ፤ ግዴታውን፣ ሥርዐቱን፣ ሕጉንና ትእዛዙን ሁልጊዜ ጠብቅ:: [2]የአምላካ ችሁን የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ተግሣጽ ይኸ ውም ግርማውን፣ ብርቱ እጁንና የተዘረጋች ክንዱን ያዩትና የተለማመዱት ልጆቻችሁ ሳይሆኑ እናንተ እንደ ሆናችሁ ዛሬ አስታ ውሱ፤ [3]በግብፅ መካከል፣ በግብፅ ንጉሥ በፈርዖንና በመላው አገሩ ላይ ያደረጋቸውን ምልክቶችና የሠራቸውን ነገሮች፣ [4]በግብፃውያን ሰራዊት፣ በፈረሶቻቸውና በሠረገሎቻቸው ላይ፣ እናንተን ባሳደዷችሁ ጊዜ በቀይ ባሕር[h] ውሃ እንዴት እንዳሰጠማቸውና እግዚአብሔር (ያህዌ) ፈጽሞ እንዴት እንዳጠፋቸው አስታውሱ፤ [5]ከምድረ በዳው አንሥቶ እዚህ እስከምትደርሱ ድረስ፣ ለእናንተ ያደረገላችሁን ያዩት ልጆቻችሁ አልነበሩም፤ [6]የሮቤል ልጅ የኤልያብ ልጆች የሆኑትን ዳታንና አቤሮንን ከነቤተሰቦቻቸው፣ ከነድንኳናቸውና ከነእንስሳታቸው በመላው እስራኤል መካከል ምድር እንዴት አፏን ከፍታ እንደ ዋጠቻቸው እነርሱ አላዩም:: [7]የእናንተ ዐይኖች ግን እግዚአብሔር (ያህዌ) ያደረጋቸውን ሥራዎች ሁሉ አይተዋል::

[8]ስለዚህ ዮርዳኖስን ተሻግራችሁ ወደምት ወርሷት ምድር ለመግባትና ለመያዝ ብርታት እንድታገኙ፣ ዛሬ እኔ የምሰጣችሁን ትእዛዞች ሁሉ ጠብቁ፤ [9]ለአባቶቻቸውና ለዘሮቻቸው እግዚአብሔር (ያህዌ) ሊሰጣቸው በማለላቸው፣ በዚያች ማርና ወተት በምታፈስው ምድር ረጅም ዕድሜ ትኖሩ ዘንድ፣ [10]የምትገቡባት ምድር እንደ ወጣህባትና ዘርህን ዘርተህባት በእግርህ ውሃ እንዳጠጣሃት የአትክልት ቦታ እንደ ግብፅ ምድር አይደለችም:: [11]ዮርዳኖስን ተሻግረህ ልትወርሳት ያለችው ምድር ግን፣ ከሰማይ ዝናብ የምትጠጣ፣ ተራሮችና ሸለቆች ያሉባት ምድር ናት:: [12]ይህች ምድር አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚንከባከባት፣ ከዓመቱ መጀመሪያ እስከ ዓመቱ መጨረሻ የአምላክህ የእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ዐይን ምንጊዜም የማይለያት ናት::

10፥10 ዘፀ33፥17
10፥12 ዘፀ20፥20፤ ዘዳ5፥32-33፤6፥5-13፤ 11፥13፤28፥47፤ 1ነገ2፥3፤3፥3፤9፥4፤ ሚክ22፥37፤ 1ጢሞ1፥5፤ መዝ100፥2፤119፥2፤ ሚክ6፥8፤
10፥13 ዘዳ4፥2፤ 5፥33፤6፥24
10፥14 ዘፀ19፥5፤ ዘዳ33፥26፤ኢሳ35፥5፤ 1ነገ8፥27፤ነህ9፥6፤ ኢዮ35፥5፤መዝ8፥3፤ 24፥1፤89፥11፤104፥3፤ 115፥16፤148፥4፤ ኢሳ19፥1፤ዕን3፥8፤ ሐሥ17፥24
10፥15 ዘኍ14፥8፤ ዘዳ4፥37፤መዝ105፥6፤ 135፥4፤ሮሜ11፥28፤ 1ጴጥ2፥9
10፥16 ዘፍ17፥11፤ ዘፀ32፥9፤13፤ ዘሌ26፥41፤ዘዳ30፥6፤ ኤር32፥39
10፥17 ዘፀ23፥8፤ ዘሌ19፥16፤ዘዳ1፥17፤ 7፥21፤ኢሱ22፥22፤ መዝ135፥5፤136፥2፤ 3፤ዳ2፥47፤11፥36፤ ሚል2፥9፤ 1ጢሞ6፥15
10፥18 ዘፀ22፥21፤ 22-24፤23፥9፤ ዘሌ19፥33፤ዘኍ10፥32፤ ዘዳ27፥19፤ ኢዮ29፥13፤ መዝ94፥6፤ኢሳ10፥2፤ ኤር49፥11
10፥19 ዘፀ22፥21፤ ዘሌ19፥34፤ዘዳ7፥12፤ 24፥19፤ሕዝ47፥22-23
10፥20 ዘፀ20፥7፤ ዘዳ11፥22፤13፥4፤30፥ 20፤ኢሱ23፥8፤ ሩት1፥14፤ 2ነገ18፥6፤ መዝ119፥31፤ ኢሳ38፥3፤ማቴ4፥10፤
10፥21 ዘፀ15፥2፤ 1ሳሙ12፥24፤ 2ሳሙ7፥23፤መዝ126፥2፤
10፥22 ዘፍ12፥2፤ 34፥30፤46፥26፤ ዘኍ10፥36፤ ሐሥ7፥14፤
11፥1 ዘሌ8፥35፤ ዘዳ6፥5
11፥2 ዘዳ31፥13፤ ዘዳ3፥24፤5፥24፤31፥13፤ መዝ78፥6፤136፥12
11፥3 ዘፀ7፥8-21

11፥4 ዘፀ14፥27፤ 15፥1፤ዘኍ21፥4 11፥6 ዘኍ16፥1-35፤ መዝ106፥16-18፤ኢሳ24፥19 11፥7 ዘዳ5፥3 11፥8 ዘዳ31፥6-7፤ 23፤ኢሱ1፥7፤ዕዝ9፥10 11፥9 ዘፀ3፥8፤ ዘዳ5፥16፤9፥5፤ 11፥10 ኢሳ11፥15፤ 37፥25 11፥11 ዘዳ8፥7፤ሕዝ36፥4፤ነህ9፥25 11፥12 1ነገ8፥29፤ 9፥3

[h]4 ዕብራይስጡ፣ ያም ሳውፍ ይለዋል፤ ይኸውም የደንገል ባሕር ማለት ነው::

ሠረተው ሙሴ ለአሮንና ለእስራኤላውያን በጸለየው ጸሎትና (9፥26-29) ስለ ታቦቱ በተጠቀሰው ክፍል (ቍ 1-5) ላይ ነው::

10፥8 *ያገለግል ዘንድ፤* የ21፥5 ማብ ይመ:: *ታቦት እንዲ ሸከም፤* የዘኍ 1፥50 ማብ ይመ::

*10፥9፤* ዘኍ 18፥20፡24 ይመ::

10፥12 *አምላክህን እግዚአብሔርን እንድትፈራው፤* የዘፍ 20፥11 ማብ ይመ:: *እንድትወደው፤* የ4፥29፡37፤ የ6፥5 ማብ ይመ::

10፥13 *መልካም እንዲሆንልህ፤* 6፥24፤ እንዲሁም የ6፥2 ማብ ይመ::

10፥16 *ልባችሁን ... ግረዙት፤* የዘፍ 17፥10 ማብ ይመ:: *ዐንገተ ደንዳና፤* 9፥6፡13፤ 31፥27 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 32፥9 ማብ ይመ::

10፥20 *ተጣበቅ፤* ሰው ከሚስቱ ጋር፣ "እንደሚጣመር" (ዘፍ 2፥24) እንዲሁም ሩት ከኑኃሚን ጋር፣ "እንደተጣበቀች" ማለት ነው (ሩት 1፥14):: 4፥4፤ 11፥22፤ 13፥4፤ 30፥20 ይመ::

10፥22 *ሰባ፤* የዘፍ 46፥26-27 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዘፀ 1፥5 ይመ:: *እንደ ሰማይ ከዋክብት፤* የ1፥10 ማብ ይመ::

*11፥2-7፤* አድማጮቹ በእግዚአብሔር የርዳታና የማዳን ሥራ ውስጥ ተካፋይ መሆናቸውን፣ ሙሴ በነገሩ ሁሉ አጽንዖት ሰጥቶታል:: በ5፥3 ላይ እንደተገለጸው እግዚአብሔር ቃል ኪዳን የገባው ከአባቶ ቻቸው ጋር ሳይሆን ከእነርሱ ጋር ነው:: በዚህ ቦታ እንደተጠቀሰው፣ የእግዚአብሔርን ታላላቅ ሥራዎች ያዩት ልጆቻቸው ሳይሆኑ እነርሱ ራሳቸው ናቸው::

11፥2 *አስታውሱ፤* የ4፥10 ማብ ይመ::

*11፥8-12፤* የ8፥7-9 ማብ ይመ::

11፥9 *ረጅም ዕድሜ ትኖሩ ዘንድ፤* የ6፥2 ማብ ይመ::

11፥10 *በእግርህ ውሃ እንዳጠጣሃት፤* በግብፅ ምድር የሚገኙ

[13]ዛሬ እኔ የምሰጣችሁን ትእዛዞች በታማኝነት ብትጠብቁ፣ ይኸውም አምላካችሁን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ብትወዱና በፍጹም ልባችሁ፣ በፍጹም ነፍሳችሁም እርሱን በማገልገል፣ በታማኝነት ብትጠብቁ፣ [14]እህልህን፣ ወይንህንና ዘይትህን እንድትሰበስብ የበልጉንና የክረምቱን ዝናብ በምድርህ ላይ በየወቅቱ አዘንባለሁ:: [15]በሜዳ ላይ ለከብቶችህ ሣር እሰጣለሁ፤ አንተም ትበላለህ፤ ትጠግባለህም::

[16]ተጠንቀቁ! አለበለዚያ ተታላችሁ ሌሎች አማልክትን ታመልካላችሁ፤ ትሰግዳላችሁም:: [17]ከዚያም *የእግዚአብሔር* (ያህዌ) *ቍጣ* በላያችሁ ይነዳል፤ እርሱም ዝናብ እንዳይዘንብ፣ ምድሪቱም ፍሬ እንዳትሰጥ ሰማያትን ይዘጋል፤ እናንተም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከሚሰጣችሁ ከመልካሚቱ ምድር ወዲያውኑ ትጠፋላችሁ:: [18]እነዚህን ቃሎቼን፣ በልባችሁና በአእምሮአችሁ አኑሯቸው፤ በእጆቻችሁ ላይ ምልክት አድርጋችሁ እሰሯቸው፣ በግምባራችሁም ላይ ይሁኑ:: [19]ልጆቻችሁንም አስተምሯቸው፤ ቤት ስትቀመጥ፣ መንገድ ስትሄድ፣ ስትተኛና ስትነሣ ስለ እነዚሁ አጫውታቸው:: [20]በቤትህ መቃኖችና በግቢህ በሮች ላይ ጻፋቸው፤ [21]ይህን ካደረጋችሁ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለአባቶቻችሁ ለመስጠት በማለላቸው ምድር የእናንተና የልጆቻችሁ ዘመን ከምድር በላይ ያሉ ሰማያትን ርቀት ያህል ይሆናል::

[22]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትወዱ ዘንድ፣ በመንገዶቹም ሁሉ ትሄዱና ከእርሱም ጋር ትጣበቁ ዘንድ እንድትከተሏቸው የምሰጣችሁን እነዚህን ትእዛዞች ሁሉ በጥንቃቄ ብትጠብቁ፣ [23]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እነዚህን አሕዛብ ሁሉ ከፊታችሁ ያስወጣቸዋል፤ እናንተም፣ ከእናንተ ይልቅ ታላላቅና ብርቱ የሆኑትን አሕዛብ ታስለቅቃላችሁ:: [24]በእግራችሁ የምትረግጡት ስፍራ ሁሉ የእናንተ ይሆናል፤ ግዛታችሁም ከምድረ በዳው እስከ ሊባኖስ፣ ከኤፍራጥስ ወንዝ አንሥቶ በስተ ምዕራብ እስካለው ባሕር[ሀ] ይደርሳል:: [25]ማንም ሰው ሊቋቋማችሁ አይችልም፤ *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሰጣችሁ ተስፋ *መሠረት ማስደንገጣችሁንና መፈራታችሁን* በምትሄዱበት በየትኛውም ምድር ሁሉ ላይ ያሳድራል::

[26]እነሆ፤ ዛሬ በረከትንና መርገምን በፊታችሁ አኖራለሁ፤ [27]በረከቱ ዛሬ የምሰጣችሁን *የአምላካችሁን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዞች ስትፈጽሙ ሲሆን፣ [28]*መርገሙ* ደግሞ፣ *የአምላካችሁን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዞች የማትፈጽሙ፣ የማታውቋቸውንም ሌሎች አማልክት ለመከተል እኔ ከማዛችሁ መንገድ የምትወጡ ከሆነ ነው:: [29]ልትወርሳት ወደ ምትሄድባት ምድር *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚያስገባህ ጊዜ በረከቱን በገሪዛን ተራራ፣ መርገሙን ደግሞ በጌባል ተራራ ላይ ታሰማለህ:: [30]እነዚህ ተራሮች የሚገኙት ከዮርዳኖስ ማዶ[ለ] ፀሓይ በምትጠልቅበት አቅጣጫ ካለው መንገድ በስተ ምዕራብ በዓረባ በሚኖሩ የከነዓናውያን ምድር ውስጥ ከጌልገላ ፊት ለፊት፣ በሞሬ ታላላቅ ዛፎች አጠገብ አይደለምን? [31]*አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጣችሁ ምድር ትገቡባትና ትወርሷት ዘንድ ዮርዳኖስን ልትሻገሩ ስለ ሆነ፣ ምድሪቱን ወርሳችሁ በምትኖሩባት ጊዜ፣ [32]ዛሬ በፊታችሁ እኔ ያስቀመጥኋቸውን ሥርዐቶችና ሕጎች ሁሉ ለመፈጸም ተጠንቀቁ::

## ብቸኛው የማምለኪያ ስፍራ

**12** የአባቶቻችሁ *አምላክ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም)፣ እንድትወርሷት በሰጣችሁ ምድር ላይ በምትኖሩባት ጊዜ ሁሉ፣ በጥንቃቄ ልትከተሏቸው የሚገባችሁ ሥርዐቶችና ሕግጋት እነዚህ ናቸው:: [2]ከምድራቸው የምታስለቅቋቸው አሕዛብ በረጅሙ ተራሮች፣ በኰረብቶችና በእያንዳንዱ ዛፍ ሥር አማልክታቸውን የሚያመልኩባቸውን ስፍራዎች ሁሉ ፈጽማችሁ አጥፉ:: [3]መሠዊያዎቻቸውን አፍርሱ፤ የማምለኪያ ዐምዶቻቸውን ሰባብሩ፤ የአሼራ ምስል ዐምዶቻቸውን በእሳት አቃጥሉ፤ የአማልክታቸውን ጣዖቶች ቈራርጣችሁ ጣሉ፤ ስማቸውንም ከእነዚያ ስፍራዎች ላይ አጥፉ::

[4]በእነርሱ *መንገድ አምላካችሁን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) አታምልኩ:: [5]ዳሩ ግን *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለስሙ ማደሪያ እንዲሆነው፣ በነገዶቻችሁ መካከል የሚመርጠውን

11÷13 ዘዳ4÷29፤ 6÷17፤10÷12፤ኤር17÷24
11÷14 ዘሌ26÷4፤ መዝ147÷8፤ኤር3÷3፤ 5÷24፤ኢዩ2÷23፤ ሐሥ14÷17፤ያዕ5÷7
11÷15 ዘሌ26÷5፤ መዝ104÷14
11÷16 ዘዳ4÷19፤ 8÷19፤29÷18፤ ኢዮ31÷9:27
11÷17 ዘሌ26÷20፤ ዘዳ4÷26፤6÷15፤9÷19፤ 28÷12:24፤1ነገ17÷1፤ 2ዜና6÷26፤7÷13፤
11÷18 ዘፀ13÷9፤ ዘዳ6÷6-8
11÷19 ዘፀ12÷26፤ ዘዳ4÷9-10፤6÷7፤ መዝ145÷4፤ ኢሳ38÷19፤ ኤር32÷39፤
11÷20 ዘዳ6÷9
11÷21 ኢዮ5÷26፤ ምሳ3÷2፤4÷10፤9÷11
11÷22 ዘዳ6÷5:17፤ 10÷20
11÷23 ዘፀ23÷28፤ ዘዳ9÷1:5
11÷24 ዘፍ2÷14፤ 15÷18፤ዘዳ1÷36፤ 12÷20፤19÷8፤ ኢያ1÷3:14÷9
11÷25 ዘፀ23÷27፤ ዘዳ2÷25፤7÷24
11÷26 ዘሌ26÷14-17፤ ዘዳ27÷13-26፤30÷1: 15:19፤መዝ24÷5፤ ሰቆ2÷17፤ዳን9÷11፤ ሐጌ1÷11፤ ሚል2÷2፤3÷9፤4÷6
11÷27 ዘዳ28÷1-14፤ መዝ24÷5
11÷28 ዘዳ4÷28፤ 13÷6:13፤29÷26፤ 1ሳሙ26÷19፤ 2ዜና24÷20፤ ኤር42÷13፤44÷16፤
11÷29 ዘዳ27÷4: 12-13፤ኢያ8÷30: 33፤መሳ9÷7፤ዮሐ4÷20
11÷30 ዘፍ12÷6፤ ኢያ4÷19፤5÷9፤9÷6፤ 10÷6፤14÷6፤15÷7፤ መሳ2÷1፤2ነገ2÷1፤ ሚክ6÷5
11÷31 ዘኍ33÷53፤ ዘዳ12÷10፤ኢያ11÷23
12÷1 ዘዳ4÷9-10፤ 6÷5፤1ነገ8÷40፤ መዝ119÷5፤ሕዝ20÷19

12÷2 ዘኍ21÷28፤ 1ነገ14÷23፤2ነገ17÷10፤ኢሳ57÷5፤ኤር2÷20፤ 3÷6:13 12÷3 ዘፀ23÷13፤32÷20፤34÷13፤ነገ11÷18፤1ነገ14÷15:23 12÷4 ቍ30፤2ነገ17÷15፤ኤር10÷2 12÷5 ቍ11:13፤ዘፀ20÷24፤ ዘዳ14÷23፤ 15÷20፤16÷2:11፤ 18÷6፤26÷2፤ 1ሳሙ2÷29፤ 2ሳሙ7÷13፤1ነገ5÷5፤ 8÷16፤9÷3፤2ዜና2÷4፤ 6÷6፤7÷12:16፤ዕዝ6÷12፤ 7÷15፤መዝ26÷8፤ 78÷68፤ዘካ2÷12

[ሀ]24 የሜዲትራንያን ባሕር ነው::
[ለ]30 ወይም፣ *ከዮርዳኖስ በስተ ምዕራብ*::

ተክሎች ውሃ የሚያገኙት ከዐባይ ወንዝ በቦይ ተስቦ ከሚመጣ ውሃ ነው፤ የከነዓን ምድር ውሃ የምታገኘው ግን ከዝናብ ነው (ቍ 11)::

*11÷13፤* የ4÷29 ማብ ይመ::

11÷14 *የበልጉንና የክረምቱን ዝናብ፤* በፓለስቲና የዝናቡ ወቅት በጥቅምት ጀምሮ በሚያዝያ ያቆማል::

11÷17 *ሰማያትን ይዘጋል፤* በከነዓን የሚኖሩ ሰዎች እንደሚያስቡት (ከሆሴ 2÷8 :17 ጋር ያነጻጽሩ)፣ እጅግ አስፈላጊውንና ወቅቱን ጠብቆ የሚመጣውን ዝናብ (ቍ 14 ይመ) የሚቈጣጠረው በኣል ሳይሆን እግዚአብሔር ነው::

*11÷18-20፤* የ6÷8-9 ማብ ይመ::

11÷22 *ትጣበቁ ዘንድ፤* የ10÷20 ማብ ይመ::

11÷24 *በእግራችሁ የምትረግጡት ስፍራ ሁሉ፤* የ1÷7 ማብ ይመ::

*11÷26-30፤* በገሪዛንና በጌባል ተራሮች ላይ የተነገሩት በረከቶችና መርገሞች በም 27-28 ላይ በሰፊው ተዘርዝረዋል::

11÷28 *የማታውቋአቸውን፤* ከዚህ በፊት አይታችኋቸውም ሆነ ሰግዳችሁላቸው የማታውቋቸውን ማለት ነው (13÷2:6:13፤ 28÷64፤ 29÷26፤ 32÷17 እንዲሁም የዘፀ 6÷3 ማብ ይመ)::

11÷30 *መንገድ፤* ምናልባት በገሊላ ባሕርና በሙት ባሕር መካከል፣ ከዮርዳኖስ ወንዝ ጋር ትይዩ ሆኖ ከሰሜን ወደ ደቡብ የተዘረጋውን መንገድ ሊሆን ይችላል:: *ዓረባ፤* የ1÷1 ማብ ይመ:: በዚያ ይኖሩ የነበሩት ከነዓናውያን በገሪዛንና በጌባል ተራሮች አካባቢ የነበረውን ስፍራ ተቈጣጥረውት ነበር:: *በሞሬ ታላላቅ ዛፎች፤* የዘፍ 12÷6 ማብ ይመ::

12÷3 *መሠዊያዎቻቸውን … የማምለኪያ ዐምዶቻቸውን … የአሼራ ምስል ዐምዶቻቸውን፤* የ7÷5 ማብ ይመ::

12÷4 *በእነርሱ መንገድ፤* ጣዖታት የሚመለኩበትን የአምልኮ ሥርዐትና የሚገለገሉበትን ዕቃ ተጠቅሞ፣ እውነተኛውን አንድ አምላክ ማምለክ ተገቢ አይደለም (ከቍ 29-31 ጋር ያነጻጽሩ)::

12÷5 *አምላካችሁ እግዚአብሔር ለስሙ ማደሪያ …*

ስፍራ እሹ፤ ወደዚያም ስፍራ ሂዱ። [6]ወደዚያም የሚቃጠሉ መሥዋዕቶቻችሁንና ሌሎች መሥዋዕቶቻችሁን፣ ዐሥራታችሁንና የእጃችሁን ስጦታ፣ ስእለቶቻችሁንና የፈቃዳችሁን ስጦታዎች፣ የቀንድ ከብት መንጋችሁን፣ የበግና የፍየል መንጋዎቻችሁን በኵራት አምጡ። [7]በዚያም *በአምላካችሁ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) *ፊት ትበላላችሁ፤ አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እናንተን በባረከበት፣ በምታደርጉት ሁሉ አንተና ቤተ ሰዎችህ ሐሤት ታደርጋላችሁ።

[8]ዛሬ እንደምናደርገው ሁሉ፣ እያንዳንዱ የሚመስለውን እንዳደረገ አታድርጉ፤ [9]ምክንያቱም ማረፊያ ወደ ሆነውና *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጣችሁ ርስት ገና አልደረሳችሁም። [10]ይሁን እንጂ ዮርዳኖስን ስትሻገሩና *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጣችሁ ምድር ስትቀመጡ፣ ያለ ሥጋት እንድትኖሩ በዙሪያችሁ ካሉት ጠላቶቻችሁ ሁሉ ያሳርፋችኋል። [11]ከዚያም *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለስሙ ማደሪያ እንዲሆን ወደሚመርጠው ስፍራ፣ እኔ የማዝዛችሁን ሁሉ፦ የሚቃጠሉ መሥዋዕቶቻችሁንና ሌሎች መሥዋዕቶቻችሁን፣ ዐሥራቶቻችሁንና የእጃችሁን ስጦታ፣ እንዲሁም *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) የተሳላችኋቸውን ምርጥ ነገሮች ሁሉ ወደዚያ ታመጣላችሁ። [12]እዚያም እናንተ፣ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻችሁ፣ ወንዶችና ሴቶች አገልጋዮቻችሁ፣ እንዲሁም የራሳቸው ድርሻ ወይም ርስት የሌላቸው በየከተሞቻችሁ የሚኖሩት ሌዋውያን በእግዚአብሔር ፊት ሐሤት አድርጉ። [13]የሚቃጠለውን መሥዋዕትህን በፈለግኸው ስፍራ ሁሉ እንዳታቀርብ ተጠንቀቅ። [14]ከነገዶችህ መካከል በአንዱ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሚመርጠው ስፍራ ብቻ የሚቃጠሉ መሥዋዕቶችህን አቅርብ፤ እዚያም እኔ የማዝዝህን ሁሉ ጠብቅ፤ [15]ሆኖም *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ መጠን፣ በየትኛውም ከተማህ፣ እንስሳትህን ሚዳቋም ሆነ ድኵላ ዐርደህ የምትፈልገውን ያህል ሥጋ ብላ፤ በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ የሆነም ሆነ ያልሆነ ሰው ከዚሁ ሥጋ ሊበላ ይችላል። [16]ደሙን ግን እንደ ውሃ መሬት ላይ አፍስሰው እንጂ አትብላው። [17]የእህልህን፣ የወይን ጠጅህንና የዘይትህን ዐሥራት፣ ወይም የቀንድ ከብት፣ የበግና የፍየል መንጋህን በኵራት፣ ወይም ለመስጠት የተሳልኸውን ወይም የፈቃድህን ስጦታ፣ ወይም የእጅህን ስጦታ፣ በከተሞችህ ውስጥ መብላት የለብህም። [18]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚመርጠው ስፍራ አንተ፣ ወንዶችና ሴቶች ልጆችህ፣ ወንድና ሴት አገልጋዮችህ፤ በከተሞችህ የሚኖር ሌዋዊም፣ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) *ፊት* ትበሉታላችሁ፤ እጅህም በነካው ነገር ሁሉ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) *ፊት* ደስ ይበልህ። [19]በምድርም ላይ በምትኖርበት ጊዜ ሁሉ ሌዋዊውን ቸል እንዳትለው ተጠንቀቅ።

[20]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሰጠህ ተስፋ መሠረት ግዛትህን ሲያሰፋልህ፣ ሥጋ አምሮህ፣ "ሥጋ መብላት እፈልጋለሁ" በምትልበት ጊዜ፣ ያሰኘህን ያህል ሥጋ መብላት ትችላለህ። [21]ስሙን ለማኖር *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የመረጠው ስፍራ ከአንተ እጅግ የራቀ ከሆነ፣ ባዘዝሁህ መሠረት ከቀንድ ከብትህ፣ ከበግና ከፍየል መንጋህ እንስሳት ማረድ ትችላለህ፤ በከተሞችህ ውስጥ የምትፈልገውን ያህል መብላት ትችላለህ። [22]ሚዳቋ ወይም ድኵላ እንደሚበላ አድርገህ ብላ፤ በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ የሆኑትና ያልሆኑት ሊበሉ ይችላሉ። [23]ደሙን ግን እንዳትበላ ተጠንቀቅ፤ ደም ሕይወት ስለ ሆነ፣ ሥጋን ከነሕይወቱ አትብላ። [24]ደሙን እንደ ውሃ በመሬት ላይ አፍስሰው እንጂ አትብላው። [25]*በእግዚአብሔር* (ያህዌ) *ፊት* ትክክል የሆነውን ነገር ስለምታደርግ፣ ለአንተም ሆነ ከአንተ በኋላ ለሚመጡት ልጆችህ መልካም እንዲሆንላቸው አትብላው።

[26]ነገር ግን የተቀደሱ ነገሮችህን ለመስጠት የተሳልሃቸውን ሁሉ ይዘህ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ወደሚመርጠው ስፍራ ሂድ። [27]የሚቃጠል መሥዋዕትህን፣ ሥጋውንም ደሙንም *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) መሠዊያ ላይ አቅርብ። የመሥዋዕትህ ደም *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) መሠዊያ ላይ ይፍሰስ፤ ሥጋውን ግን መብላት ትችላለህ። [28]*በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) *ፊት* መልካምና ትክክል የሆነውን ነገር ስለምታደርግ፣ ለአንተና ከአንተም በኋላ ለሚመጡት ልጆችህ ለዘላለም መልካም እንዲሆንላችሁ፣ እኔ የምሰጥህን

12፥6 ዘፍ28፥20፤ ዘሌ27፥30፤ኢሱ22፥27፤ ኢሳ66፥20
12፥7 ዘፀ18፥12፤ ዘሌ23፥40፤ መክ3፥12-13፤ 5፥18-20፤ኢሳ62፥9
12፥8 መሳ17፥6፤ 21፥25
12፥9 ዘፀ33፥14፤ ዘዳ3፥20፤4፥21፤ መዝ95፥11፤ሚክ2፥10
12፥10 ዘፀ33፥14፤ ዘዳ11፥31፤
12፥11 ቍ5፤ ዘሌ1፥3፤ኢሱ22፥23
12፥12 ቍ7፤ ዘኍ18፥20፤ ዘዳ26፥11-13
12፥13 ቍ5
12፥14 ቍ11
12፥15 ቍ22፤ ዘዳ14፥5፤15፥22
12፥16 ቍ23-24፤ዘፍ9፥4፤35፥14፤ ዘሌ17፥13፤ዘዳ15፥23፤ 1ዜና11፥18፤ሕር7፥18፤ ዮሐ19፥34፤ ሐሥ15፥20፤
12፥17 ቍ26፤ ዘሌ27፥30፤ዘኍ18፥12፡ 19፤ዘዳ14፥23፤15፥20
12፥18 ቍ5፡7፡12፤ ዘዳ14፥23፡26፤15፥20፤ ነህ8፥10፤ መክ3፥12-13፤5፥18-20
12፥19 ቍ12፤ ዘዳ14፥27፤ነህ13፥10፤ ሚል3፥8
12፥20 ዘፍ15፥8፤ ዘፀ16፥3፤34፥24፤ ዘዳ11፥24
12፥21 ዘሌ17፥4፤ ዘዳ14፥24፤
12፥22 ቍ15
12፥23 ዘሌ7፥26፤ ሕዝ33፥25
12፥24 ቍ16
12፥25 ቍ28፤ ዘፀ15፥26፤ዘዳ4፥40፤ 13፥18፤1ነገ11፥38፤ 2ነገ12፥2
12፥26 ቍ17፤ ዘኍ5፥9-10
12፥27 ዘሌ1፥13፤ 3፥1-17
12፥28 ዘዳ4፥40፤ መክ8፥12

*የሚመርጠውን ስፍራ፤* እስራኤላውያን በምድረበዳ በሚጓዙበት ወቅት የእግዚአብሔር ማደሪያ በመሆን ያገለገለው የመገናኛው ድንኳን፣ ራሱ እግዚአብሔር ሊያድርበት በመረጠው ስፍራ በከነዓን ይተከላል። ሙሴ እስራኤላውያን የተስፋዪቱን ምድር እንዲወርሱና በዚያም መኖሪያውን እንዲያደርጉ በሚያሳስባቸው ጊዜ የአምልኮ ስፍራቸውን በአንድ ማእከላዊ ቦታ ማድረግ እንዳለባቸው አበክሮ አሳውቆአቸዋል፤ ባንጻሩም ከነዓናውያን በርካታ የማምለኪያ ቦታ ነበራቸው (ቍ 11፡14 18፡21፡26፤ 14፥23-24፤ 16፥2፡6፡11፤ 26፥2 ይመ)።

*12፥6፤* ቍ 11 ይመ። እንዲሁም፣ "የብሉይ ኪዳን መሥዋዕቶች" የሚለውን ስንጠረዥ በገጽ 151 ላይ ይመ።

12፥8 *ዛሬ እንዳደረግነው ሁሉ፤* እስራኤላውያን በምድረበዳ በሚንከራተቱበትና ከባላጋራዎቻቸው ጋር ፍልሚያ በሚያደርጉበት ወቅት የመሥዋዕት አቀራረቡን ሥርዐት በሚገባ መከተል አልቻሉም ነበር። ሙሴ ምድሪቱን በሚወርሱበትና በዚያም በሚኖሩበት ወቅት እንዴት መሥዋዕታቸውን ማቅረብና መኖር እንዳለባቸው መመሪያ እየሰጣቸው ነበር (ቍ 10-14)። *እያንዳንዱ እንደሚመስለው፤* የመሳ 17፥6 ማብ ይመ።

12፥9 *ማረፊያ ወደ ሆነው፤* የ3፥20 ማብ ይመ።

12፥11 *ለስሙ ማደሪያ፤* "ለራሱ ማደሪያ" ከሚለው ጋር ይመሳሰላል። የዘፀ 3፥13-15 ማብ ይመ።

12፥12 *ርስት የሌላቸው ... ሌዋውያን፤* 10፥9፤ ዘኍ 18፥20፡24 ይመ። *በእግዚአብሔር ፊት ሐሤት አድርጉ፤* ዕብራውያን በተስፋዪቱ ምድር ተደላድለው በሚኖሩበት ወቅት በእግዚአብሔር በረከት ላይ የተመሠረተ ደስታ የዕለት ተዕለት ኑሮአቸውና አምልኮአቸው አንዱና ትልቁ ገጽታ ነው (ቍ 7፥18)።

12፥13 *በፈለግኸው ስፍራ ሁሉ እንዳታቀርብ፤* መሥዋዕቶችና ስጦታዎች ሁሉ ለእግዚአብሔር መቅረብ ያለባቸው የአምልኮ ማእከል በሆነው በማደሪያው ድንኳን እንጂ፣ በተለያዩ የከነዓናውያን የበኣል አምልኮ ስፍራዎች አይደለም።

12፥16፡24 *ደሙን ... አትብላው፤* የዘፍ 9፥4፤ እና የዘሌ 17፥11 ማብ ይመ።

እነዚህን ደንቦች ሁሉ በጥንቃቄ ፈጽማቸው::

29የምትወርሯቸውንና የምታስለቅቋቸውን አሕዛብ አምላካችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከፊታችሁ ያስወግዳቸዋል፤ ባስወጣችኋቸውና በምድራቸው በተቀመጣችሁ ጊዜ ግን፣ 30ከፊትህ ከጠፉ በኋላ፣ "እነዚህ ሕዝቦች አማልክታቸውን የሚያመልኩት እንዴት ነው? እኔም እንደ እነርሱ አደርጋለሁ" ብለህ በመጠየቅ እንዳ ትጠመድ ተጠንቀቅ:: 31አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) በእነርሱ መንገድ ፈጽሞ አታምልክ፤ ምክንያቱም አማልክታቸውን ሲያመልኩ እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚጸየፈውን ሁሉንም ዐይነት ነገር ያደርጋሉና፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን እንኳ ለአማልክታቸው መሥዋዕት አድርገው ያቃጥላሉ::

32እኔ ያዘዝሁህን ሁሉ ጠብቅ፤ አትጨምርበት፤ አትቀንስለትም::

## ሌሎች አማልክትን ማምለክ

13 ነቢይ ወይም ሕልም ዐላሚ ከመካከልህ ተነሥቶ ምልክት ወይም ድንቅ አደርጋለሁ ቢልህ፣ 2የተናገረው ምልክት ወይም ድንቅ ቢፈጸም፣ "አንተ የማታውቃቸውን ሌሎች አማልክት እናምልካቸው" ቢልህ፣ 3አምላካችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በፍጹም ልባችሁና በፍጹም ነፍሳችሁ ትወዱት እንደ ሆን ያውቅ ዘንድ ሊፈትናችሁ ነውና፣ የዚያን ነቢይ ቃል ወይም ሕልም ዐላሚውን አትስማ:: 4አምላካችሁን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ተከተሉት፤ ፍሩት፤ ትእዛዞቹንም ጠብቁ፤ ታዘዙት፤ አገልግሉት፤ ከእርሱም ጋር ተጣበቁ:: 5ከግብፅ ባወጣችሁና ከባርነት ምድር በዋጃችሁ በአምላካችሁ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ላይ እንድታምፁ ተናግሯልና፣ አምላካችሁ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትከተሉት ካዘዛችሁ መንገድ እንድትመለሱ አድርጓልና፣ ያ ነቢይ ወይም ሕልም አላሚ ይገደል፤ ስለዚህ ክፉውን ከመካከልህ አስወግድ:: 6የእናትህ ልጅ ወንድምህ፣ ወንድ ወይም ሴት ልጅህ፣ ወይም የምትወዳት ሚስትህ ወይም የልብ ጓደኛህ፣ "ሄደን ሌሎች አማልክትን እናምልክ" (አንተም ሆንህ አባቶችህ የምታውቋቸውን አማልክት፣) ብሎ በስውር ሊያስትህ ቢሞክር፣ 7በቅርብም ሆነ በሩቅ፣ ከአንዱ የምድር ጫፍ እስከ ሌላው ድረስ በዙሪያህ ያሉትን የአሕዛብ አማልክት እናምልክ ቢልህ፣ 8እሺ አትበለው፤ ወይም አታዳምጠው፤ አትራራለት፤ አትማረው፤ ወይም አትሸሽገው:: 9ያለማመንታት ግደለው፤ እርሱንም ለመግደል በመጀመሪያ የአንተ እጅ፣ ከዚያም በኋላ የሕዝቡ ሁሉ እጅ ይነሣ:: 10የባርነት ምድር ከሆነው ከግብፅ ካወጣህ ከአምላክህ ከእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ሊያርቅህ ፈልጎአልና እስኪሞት ድረስ በድንጋይ ውገረው:: 11ከዚያም እስራኤል ሁሉ ሰምተው ይፈራሉ፤ ከመካከልህም ማንም እንደዚህ ያለውን ክፉ ነገር ዳግም አያደርግም::

12አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትኖርባቸው ከሚሰጥህ ከተሞች ባንዲቱ ውስጥ እንዲህ ሲባል ብትሰማ፣ 13ክፉ ሰዎች ከመካከላችሁ ተነሥተው አንተ የማታውቃቸውን፣ "ሌሎች አማልክትን ሄደን እናምልክ" በማለት የከተማቸውን ሕዝብ እያሳቱ ቢሆን፣ 14ጉዳዩን አጣራ፤ መርምር፤ በሚገባም ተከታተል፤ ነገሩ እውነት ሆኖ ከተገኘና ይህ አስጸያፊ ነገር በመካከልህ መፈጸሙ ከተረጋገጠ፣ 15በዚያች ከተማ የሚኖሩትን ሁሉ በሰይፍ ግደላቸው፤ ከተማዪቱን ከነሕዝቧና ከነቀንድ ከብቷ ፈጽሞ ደምስሳት°:: 16በከተማዪቱ የተገኘውን የምርኮ ዕቃ ሁሉ በአደባባይዋ መካከል ላይ ሰብስበህ፣ ከተማዪቱን ከነምርኮዋ እንዳለ ለአምላክህ ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚቀርብ መሥዋዕት አድርገህ በሙሉ አቃጥል:: ለዘላለም እንደ ፈረሰች ትቅር፤ ተመልሳም አትሠራ:: 17እግዚአብሔር (ያህዌ) ከቁጣው ይመለስ ዘንድ እርም ከሆኑ ነገሮች በእጅህ አይገኝ°፤ እርሱ ምሕረቱን ያሳይሃል፤ ይራራልሃል፤ ለአባቶችህ በመሐላ ተስፋ በሰጠው መሠረት ቍጥርህን ያበዛዋል፤ 18ይህም የሚሆነው ዛሬ እኔ የምሰጥህን ትእዛዞቹን ሁሉ በመጠበቅና መልካም የሆነውን በአምላክህ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት በማድረግ ለአምላክህ ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ስለ ታዘዝህለት ነው::

## ንጹሕና ንጹሕ ያልሆነ ምግብ

14፥3-20 ተጓ ምብ - ዘሌ 11 1-23

14 እናንተ የአምላካችሁ የእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ልጆች ናችሁ፤ ለሞተ ሰው ሰውነታችሁን አትብጩ፤ ከግንባራችሁ በላይ ያለውን ጠጕር አትላጩ፤ 2ምክንያቱም አንተ ለአምላክህ ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ቅዱስ ሕዝብ

12፥29 ዘጸ6፥10፤ ኢሱ23፥4፤
12፥30 ቍ41 ዘፀ10፥7፤
12፥31 ዘሌ18፥21፡ 25፤2ነገ13፥27
12፥32 ዘዳ4፥2፤ ራእ22፥18-19
13፥1 ዘፍ20፥3፤ ኤር23፥25፤27፥9፤ 29፥8፤ማቴ24፥24፤ ማር13፥22፤2ተሰ2፥9
13፥2 ዘዳ11፥28፤ 18፥22፤1ሳሙ2፥34፤ 10፥9፤2ነገ19፥29፤ 20፥9፤ኢሳ7፥11፤
13፥3 ዘፍ22፥1፤ ዘዳ6፥5፤1ሳሙ28፥6፡ 15፤1ነገ13፥18፤ 22፥22-23፤ ኤር29፥31፤43፥2፤ ሕዝ13፥9፤1ቆሮ11፥19፤ 2ጴጥ2፥1
13፥4 ዘዳ6፥13፤ 10፥20፤2ነገ23፥3፤ 2ዜና34፥31፤ መዝ5፥7፤2ዮሐ1፥6
13፥5 ቍ10፤ ዘፀ21፥12፥12፤ 22፥20፤ ዘዳ4፥19፤17፥7፡12፤1 9፥19፤24፥7፤ መሳ20፥13፤1ቆሮ5፥13
13፥6 ዘዳ11፥28፤ 17፥2-7፤29፥18
13፥8 ዘዳ7፥2፤ ምሳ1፥10
13፥9 ቍ5፤ዘሌ24፥14
13፥10 ዘፀ20፥3
13፥11 ዘዳ17፥13፤ 19፥20፤21፥21፤ 1ጢሞ5፥20
13፥13 መሳ19፥22፤ 20፥13፤1ሳሙ2፥12፤ 10፥27፤11፥12፤ 25፥17፤1ነገ21፥10
13፥14 ዘዳ17፥4፤ መሳ20፥12
13፥15 ዘፀ22፥20፤ ኢሳ24፥6፤34፥5፤ 43፥28፥47፥6፤ ሰቆ2፥6፤ዳን9፥11፤ ዘካ8፥13፤ሚል4፥6፤
13፥16 ዘዳ7፥25፡ 26፤ኢሱ6፥24፤ 8፥28፤2ነገ25፥9፤ ኢሳ7፥16፤17፥1፤ 24፥10፤25፥2፤27፥10፤ 32፥14፡19፤37፥26፤ ኤር39፥8፤49፥2፤ 52፥13፤ሕዝ16፥41፤ ሚክ1፥6
13፥17 ዘፍ12፥2፤
13፥14፤26፥24፤43፥14፤ዘፀ32፥12፤ ዘኍ25፥4፤ ዘዳ7፥13፤30፥3፤
13፥18 ዘዳ12፥25 14፥1 ዮሐ1፥12፤ሮሜ8፥14፤ 9፥8 14፥2 ዘፍ28፥14፤ዘፀ8፥22፤22፥31፤ዘሌ20፥26፤ዘዳ7፥6፤ኢሳ6፥13፤ ሚል2፥15፤ሮሜ12፥1፤

°15:17 የዕብራይስጡ ቃል አንድን ነገር ወይም አንድን ሰው ሙሉ በሙሉ በማጥፋት ለእግዚአብሔር መስጠትን የሚያሳይ ነው::

12፥31 *ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን ... መሥዋዕት አድርገው ያቃጥላሉ፤* 18፥10 ይመ፤ እንዲሁም የዘሌ 18፥21 ማብ ይመ::

12፥32 *አትጨምርበት፤ አትቀንስለትም፤* የ4፥2 ማብ ይመ::

*13፥1-5፤* የአንድ ትንቢት እውነተኛነት የሚረጋገጠውና የሚታወቀው ትንቢቱ እንደተነገረው ሲፈጸም ነው (18፥21-22)፤ ሆኖም በዚህ ቦታ የተሰጠው መመሪያ፣ በልዩ ችሎታ መጪውን ዘመን ከወዲሁ ከሚተነብዩና በአጋጣሚ ከሚፈጸም የሐሰተኞች ነቢያት ትንቢት እንድንጠበቅ የሚያሳስብ ነው::

13፥3 *በፍጹም ልባችሁ፤* የ4፥29 ማብ ይመ:: *ሊፈትናችሁ፤* የዘፍ 22፥1 ማብ ይመ::

13፥4 *ተጣበቁ፤* የ10፥20 ማብ ይመ::

13፥5 *ነቢይ ... ይገደል፤* 18፥20፤ ኤር 28፥15-17 ይመ:: *ክፉውን ከመካከልህ አስወግድ፤* ይህ ትእዛዝ 17፥7፤ 19፥19፤ 21፥21፤ 22፥21፡24፤ 24፥7 ላይ ተደጋግሞ ተጠቅሶአል፤ ሐሳቡም በ1ቆሮ 5፥13 ላይ ይገኛል:: ይህ መመሪያ የተሰጠበት ዋና ዐላማ ክፉ አድራጊዎችንና ክፉን ለማስወገድ ነው::

13፥13 *ክፉ ሰዎች፤* 1ሳሙ 1፥16፤ 2፥12፤ 25፥17 ይመ:: በዚህ ቦታ የምናገኘው የዕብራይስጥ ቃል በሌሎች ቦታዎችም ላይ ለምሳሌ በ1ሳሙ 10፥27፤ 30፥22፤ 1ነገ 21፥10፡13፤ ምሳ 6፥12 ላይ ጉብቶ ይገኛል:: ከጊዜ በኋላ ይህ ቃል (በዕብራይስጥ "ቤሊያል") የክፉትና የዐመፅ ባለቤት ለሆነው ለሰይጣን ተሰጥቶአል (2ቆሮ 6፥15)::

13፥15 *ፈጽሞ ደምስሳት፤* የ2፥34 ማብ ይመ::

14፥1 *ሰውነታችሁን አትንጩ፤* ይህን ማድረግ በአረማውያን ሃይማኖት የተለመደ ነው (1ነገ 18፥28 ይመ):: *ፊት ያለውን የራሳችሁን ጠጕር አትላጩ፤* በሐዘን ጊዜ ከፊት ለፊት ያለውን ጠጕር መላጨት በከነዓን የተለመደ ነበር::

14፥2፡21 *ለአምላክህ ለእግዚአብሔር ቅዱስ፤* የዘሌ 11፥44 ማብ ይመ:: ንጹሕና ንጹሕ ያልሆኑ ምግቦችን በተመለከተ የተሰጠው

ነህ፤ ለራሱ የተለየ ሕዝብ እንድትሆንለት እግዚአብሔር (ያህዌ) በምድር ላይ ከሚኖሩ ሕዝቦች ሁሉ አንተን መርጦሃል።

[3]ማናቸውንም ርኩስ ነገር አትብላ። [4]የምትበሏቸው እንስሳት እነዚህ ናቸው፤ በሬ፣ በግ፣ ፍየል፣ [5]ዋላ፣ ድኵላ፣ ሰስ፣ የበረሓ ፍየል፣ ዋሊያ፣ ሚዳቋ፣ አጋዘን*። [6]ሰኰናው ስንጥቅ የሆነውን፣ ለሁለት የተከፈለውንና የሚያመሰኳ ማናቸውንም እንስሳ ብላ። [7]ነገር ግን ከሚያመሰኩት ወይም ሰኰናቸው ከተሰነጠቀ እንስሳት መካከል ግመልን፣ ጥንቸልንና ሽኮኮን አትብሉ፤ እነርሱ ቢያመሰኩ እንኳ፣ ሰኰናቸው የተሰነጠቀ ባለመሆኑ፣ በሥርዐቱ መሠረት በእናንተ ዘንድ ርኩሶች ናቸው። [8]ዐሳማም እንደዚሁ ርኩስ ነው፤ ምንም እንኳ ሰኰናው የተሰነጠቀ ቢሆንም፣ ስለማያመሰኳ፣ እርሱ ለእናንተ ንጹሕ አይደለም፤ የእነዚህን ሥጋ አትብሉ፤ ጥምባቸውንም አትንኩ።

[9]በውሃ ውስጥ ከሚኖሩ ፍጡራን ሁሉ ክንፍና ግልፋፊ ያለውን ማናቸውንም ብሉ፤ [10]ክንፍና ግልፋፊ የሌለውን ግን አትብሉ፤ ለእናንተ ርኩስ ነው።

[11]ንጹሕ የሆነውን ወፍ ሁሉ መብላት ትችላላችሁ። [12]የሚከተሉትን ግን አትበሉም፤ እነርሱም፦ ንስር፣ ገዴ፣ ዓሣ አውጪ፣ [13]ጭልፊት፣ ጭላት፣ ማናቸውም ዐይነት አድኖ በል አሞራ፣ [14]ማናቸውም ዐይነት ቁራ፣ [15]ሰጎን፣ ጠላቋ፣ ዝዪ፣ ማናቸውም ዐይነት በቋል፣ [16]ጉጉት፣ ጋጋኖ፣ የውሃ ዶሮ፣ [17]ይብራ፣ ጥንብ አንሣ አሞራ፣ እርኩም፣ [18]ሽመላ፣ ማናቸውም ዐይነት ሳቢሳ፣ ጅንጅላቴ ወፍና የሌሊት ወፍ ናቸው።

[19]ክንፍ ያላቸው ጥቃቅን ነፍሳት ሁሉ ለእናንተ ርኩስ ናቸው፤ እነርሱን አትብሏቸው። [20]ንጹሕ የሆነውን ማናቸውንም ክንፍ ያለውን ፍጡር ግን ብሉ።

[21]አንተ ግን ለአምላክህ ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ቅዱስ ሕዝብ ነህና የሞተውን ሁሉ አትብላ፤ ከከተሞችህ በአንዲቱ ለሚኖር መጻተኛ ስጠው፤ ይብላውም፤ ለውጭ አገር ሰው ሽጠው። የፍየልን ግልገል በእናቱ ወተት አትቀቅል።

## ዐሥራት

[22]በየዓመቱ ከእርሻህ ከምታገኘው ምርት ከዐሥር አንዱን እጅ ለይተህ አስቀምጥ። [23]ምን ጊዜም አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ማክበር ትማር ዘንድ፣ የአዲሱን ወይን ጠጅህንና የዘይትህን ዐሥራት፣ የቀንድ ከብትህን፣ የበግና የፍየል መንጋህን በኵራት ስሙ እንዲጠራበት በሚመርጠው ስፍራ፣ በአምላክህ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ብላ። [24]ነገር ግን አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባርኮህ ሳለ፣ መንገዱ ቢርቅብህና እግዚአብሔር (ያህዌ) የስሙ ማደሪያ ይሆን ዘንድ የሚመርጠው ስፍራ ከአንተ እጅግ ከመራቁ የተነሣ ዐሥራትህን ወደዚያ ቦታ ማድረስ ካልቻልህ፣ [25]ዐሥራትህን በብር ለውጥ፤ ብሩንም ይዘህ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚመርጠው ስፍራ ሂድ። [26]በብሩም ደስ ያለህን ሁሉ ማለትም የቀንድ ከብት፣ በግ፣ የወይን ጠጅ ወይም ሌላ ብርቱ መጠጥ ወይም የምትሻውን ሁሉ ግዛበት። ከዚያም አንተና ቤተሰብህ በአምላክህ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት በዚያ ትበላላችሁ፤ ሐሤትም ታደርጋላችሁ። [27]የራሱ ድርሻ ወይም ርስት ስለሌለው በከተሞችህ የሚኖረውን ሌዋዊ ቸል አትበለው።

[28]በየሦስት ዓመቱ መጨረሻ የዚያን ዓመት ሰብል ዐሥራት በሙሉ አውጥተህ በከተሞችህ ውስጥ አከማች። [29]ይህን የምታደርገው የራሱ ድርሻ ወይም ርስት የሌለው ሌዋዊና መጻተኛ፣ በከተሞችህ የሚኖሩ አባት የሌላቸውና መበለቶች መጥተው እንዲበሉና እንዲጠግቡ፣ አንተንም አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጅህ ሥራ ሁሉ እንዲባርክህ ነው።

## ዕዳ የሚተውበት ዓመት

15፥1-11 ማመ - ዘሌ 25፥8-38

**15** በየሰባቱ ዓመት መጨረሻ የዕዳ ምሕረት አድርግ። [2]አፈጻጸሙም እንደሚከተለው ነው፤ እያንዳንዱ አበዳሪ ለእስራኤላዊ ባልንጀራው ያበደረውን ይተውለት፤ እግዚአብሔር (ያህዌ) የዕዳ ምሕረት አውጆአልና፣ አበዳሪው፣ እስራኤላዊ ባልንጀራውን ወይም ወንድሙን ዕዳውን እንዲከፍለው አይጠይቀው። [3]ለባዕድ ያበደርኸውን መጠየቅ ትችላለህ፤ ወንድምህ ከአንተ የተበደረውን ማናቸውንም ዕዳ ግን ተወው። [4]ይሁን እንጂ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ትወርሳት ዘንድ ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድር ውስጥ አብዝቶ ስለሚባርክህ፣ በመካ

*5 በዚህ ስፍራ የተጠቀሱት አንዳንድ አዕዋፍና እንስሳት ማንነታቸው በትክክል አይታወቅም።

14፥3 ሕዝ4፥14
14፥4 ዘሌ7፥23፤ ሐሥ10፥14፤
14፥5 ዘዳ12፥15፤ ኢዮ39፥1፤መዝ104፥18
14፥8 ዘሌ5፥2
14፥13 ዘፍ1፥11፤ ኢሳ34፥15
14፥14 ዘፍ8፥7
14፥17 መዝ102፥6፤ ኢሳ13፥21፤14፥23፤ 34፥11፤ሶፎ2፥14
14፥20 ዘሌ20፥25
14፥21 ቈላ2፤ ዘፀ23፥19፤ ዘሌ11፥39፤
14፥22 ዘፍ14፥20፤ ዘኍ18፥21፤ዘሌ27፥30፤
14፥23 ዘዳ4፥10፤ 12፥5፡17፡18፤1ነገ3፥2፤ መዝ4፥7፤22፥23፤ 33፥8፤ሚል2፥5
14፥25 ማቴ21፥12፤ ዮሐ2፥14
14፥26 ዘሌ10፥9፤ 23፥40፤ዘዳ12፥18፤ መክ10፥16-17
14፥27 ዘኍ18፥20፤ 26፥62፤ዘዳ12፥19፤ 18፥1-2
14፥28 ዘሌ27፥30፤ ዘዳ26፥12
14፥29 ዘፍ47፥22፤ ዘኍ26፥62፤ዘዳ6፥11፤ 15፥10፤16፥11፤ 24፥19-21፤መዝ41፥1፤ 94፥6፤ ምሳ22፥9፤ ኢሳ1፥17፤58፥6፤ ሚል3፥10
15፥1 ዘዳ31፥10፤ ነህ10፥31
15፥3 ዘፍ31፥15፤ ዘዳ23፥20፤28፥12፤ ሩት2፥10

ሕግ፣ እግዚአብሔር አስጸያፊና ርኩስ ናቸው ብሎ ከለያቸው ነገሮች እስራኤላውያንን ለመለየት ታስቦ ነው።

14፥2 *የተለየ ሕዝብ፤* የዘፀ 19፥5 ማብ ይመ።

*14፥3-21፤* ንጹሕና ንጹሕ ያልሆኑ ምግቦችን አስመልክቶ በዘሌ 11 ላይ በሰፊው ተገልጾአል (በዚያው ያለውን ማብ ይመ)።

14፥21 *የሞተ ሁሉ አትብላ፤* ደም መብላት የተከለከለው የሞተ ከብት ደም ተሚጦ ከእንስሳው ስለማይወጣ ነው (12፥16፡24፤ እንዲሁም የዘፍ 9፥4፤ የዘሌ 17፥11 ማብ ይመ)። *የፍየልን ግልገል በእናቱ ወተት አትቀቅል፤* የዘፀ 23፥19 ማብ ይመ።

*14፥22-29፤* ዘኍ 18፥21-29 ይመ። ሁለቱ ክፍሎች አንድ ላይ ሲታዩ ከዚህ የሚከተለውን ያመለክታሉ፤ (1) እስራኤላውያን ሁሉ በየዓመቱ ከሚያመርቱት ሰብል አንድ ዐሥረኛው ተወስዶ የእግዚአብሔር ማደሪያ በሚገኝበት ማእከላዊ ስፍራ ለሌዋውያን ይከፋፈላል፤ (2) በዚያን ጊዜ፣ በመጀመሪያው ክብረ በዓል እስራኤላውያን ሁሉ ከዐሥራቱ የተወሰነውን ወስደው ይመገባሉ፤ (3) የቀረው ትልቁ ድርሻ ለሌዋውያን ይሆናል፤ (4) በየሦስት ዓመቱም፣ በየከተሞቹ ዐሥራት ተሰብስቦ ይከማቻል፤ ከዚያም ለሌዋውያንና ለችግረኞች ማለትም ለመጻተኞች፣ ለድኻ አደጎችና ለመበለቶች ይከፋፈላል (26፥12 ይመ)፤ (5) ሌዋውያን በበኩላቸው ከሚያገኙት ዐሥራት አንድ ዐሥረኛውን ለእግዚአብሔር ይሰጣሉ፤ የዘሌ 27፥30 ማብ ይመ።

14፥22 *ከዐሥር አንዱን እጅ ለይተህ ማስቀመጥ፤* የዘፍ 14፥20፤28፥22 ማብ ይመ።

14፥23 *ስሙ እንዲጠራበት በሚመርጠው ስፍራ፤* የ12፥5 ማብ ይመ።

14፥25 *ብር፤* በዚያን ዘመን የመገበያያው ገንዘብ እንዲህ እንደ አሁኑ ዘመን ሳንቲም ሳይሆን፣ የተለያየ ክብደት ያለው ቍር ጥራጭ ጥሬ ብር ነበር (የዘፍ 20፥16 ማብ ይመ)።

15፥1 *በየሰባት ዓመት፤* ዘፀ 23፥10-11፤ ዘሌ 25፥1-7 ይመ።

15፥3 *ለሌላ አገር ሰው ያበደርኸውን መጠየቅ፤* በሰባተኛው ዓመት የዕርሻ ቦታችሁን አሳርፉ የሚለውን ትእዛዝ የመጠበቅ ግዴታ ስለሌለበት፣ አንድ የውጭ አገር ሰው ያለበትን ዕዳ እንዲከፍል ቢጠየቅ ዕዳውን የመክፈል ዐቅም ሊኖረው ይችላል።

ከልህ ድኻ አይኖርም፤ ⁵ይህ የሚሆነውም *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፈጽመህ ስትታዘዝና ዛሬ የምሰጥህን እነዚህን ትእዛዞች ሁሉ በጥንቃቄ ስትከተል ብቻ ነው። ⁶*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሰጠህ ተስፋ መሠረት ስለሚባርክህ፣ አንተ ለብዙ አሕዛብ ታበድራለህ እንጂ ከማንም አትበደርም፤ ብዙ አሕዛብን ትገዛለህ እንጂ ማንም አንተን አይገዛህም።

⁷*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ ምድር ላይ ካሉት ከተሞች በአንዲቱ ውስጥ ድኻ ቢኖር፣ በድኻ ወንድምህ ላይ ልብህን አታጨክንበት፤ ወይም እጅህን ወደ ኋላ አትሰብስብበት። ⁸ይልቁንስ እጅህን ፍታለት፤ የሚያስፈልገውንም ሁሉ ቅር ሳይልህ አበድረው። ⁹“ዕዳ የሚሠረዝበት ሰባተኛው ዓመት ተቃርቦአል” የሚል ክፉ ሐሳብ አድሮብህ፣ በችግረኛ ወንድምህ ላይ እንዳትጨክንና ምንም ሳትሰጠው እንዳትቀር፣ እርሱም በአንተ ላይ ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጮኾ በደለኛ እንዳትሆን ተጠንቀቅ! ¹⁰በልግስና ስጠው፤ ስትሰጠውም ልብህ አይጸጸት፤ ከዚህም የተነሣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሥራህ ሁሉና እጅህ ባረፈበት በማናቸውም ነገር ይባርክሃል። ¹¹በምድሪቱ ላይ ድኾች ምንጊዜም አይጠፉም፤ ስለዚህ በዚያ ለሚኖሩ ወንድሞችህ፣ ለድኾችና ለችግረኞች እጅህን እንድትዘረጋ አዝሃለሁ።

## አገልጋዮችን ዐርነት ማውጣት

15፥12-18 ተጓ ምብ - ዘፀ 21፥2-6
15፥12-18 ማመ - ዘሌ 25፥38-55

¹²ወገንህ የሆነ ዕብራዊ ወንድን ወይም ሴትን ገዝተህ ስድስት ዓመት ካገለገለህ፣ በሰባተኛው ዓመት ዐርነት አውጣው። ¹³በምታሰናብተውም ጊዜ ባዶ እጁን አትስደደው። ¹⁴ከመንጋህ፣ ከዐውድማህና ከወይን መጭመቂያህ በልግስና ስጠው፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በባረከህ መጠን ስጠው። ¹⁵አንተም ራስህ በግብፅ ባሪያ እንደ ነበርህና *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንደ ተቤዠህ አስታውስ፤ ይህን ትእዛዝ ዛሬ የምሰጥህም በዚሁ ምክንያት ነው።

¹⁶ነገር ግን አገልጋይህ፣ አንተንና ቤተ ሰብህን ከመውደዱና ከአንተም ጋር ደስተኛ ሆኖ ከመኖሩ የተነሣ፣ “ከአንተ መለየት አልፈልግም” ቢልህ፣ ¹⁷ጆሮውን ከቤትህ መዝጊያ ላይ በማስደገፍ በወስፌ ትበሳዋለህ፤ ከዚያም ዕድሜ ልኩን አገልጋይህ ይሆናል። በሴት አገልጋይህም ላይ እንደዚሁ አድርግ።

¹⁸አገልጋይህን ዐርነት ማውጣቱ ከባድ መስሎ አይታይህ፤ የስድስት ዓመት አገልግሎቱ፣ አንድ የቅጥር ሠራተኛ የሚሰጠው አገልግሎት ዕጥፍ ነውና። *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በምታደርገው ነገር ሁሉ ይባርክሃል።

## የእንስሳት በኵራት

¹⁹የቀንድ ከብት፣ የበግና የፍየል መንጋችህን ተባዕት በኵር ሁሉ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ቀድስ። የበሬህን በኵር አትሥራበት፤ የበግህንም በኵር አትሸልት፤ ²⁰እርሱ በሚመርጠው ስፍራ አንተና ቤተ ሰብህ በየዓመቱ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ትበሉታላችሁ። ²¹አንድ እንስሳ እንከን ካለበት፣ አንካሳ ወይም ዕውር፣ ወይም ደግሞ ማናቸውም ዐይነት ከባድ ጕድለት ያለበት ከሆነ፣ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አትሠዋው፤ ²²በየከተሞችህም ትበላዋለህ፤ በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ የሆነውም ሆነ ያልሆነው ሰው፣ እንደ ድኵላ እንደ ዋላ ይበላዋል። ²³ደሙን ግን እንደ ውሃ መሬት ላይ አፍስሰው እንጂ አትብላው።

## ፋሲካ

16፥18-ተጓ ምብ - ዘፀ 12፥14-20፤ ዘሌ 23 4-8፤ ዘኍ 28፥16-25

**16** *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በአቢብ ወር ከግብፅ በሌሊት ስላወጣህ፣ የአቢብን ወር ጠብቅ፤ *የአምላክህን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ፋሲካ አክብርበት። ²*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለስሙ ማደሪያ ይሆን ዘንድ በሚመርጠው ስፍራ ከበግና ከፍየል ወይም ከመንጋህ አንዱን

15፥4 ዘዳ 28፥8
15፥5 ዘፀ15፥26፤ ዘዳ7፥12፤28፥1
15፥6 ዘዳ28፥12-13፡44
15፥7 ቍ፡11፤ ማቴ26፥11፤ 1ዮሐ3፥17
15፥8 ማቴ5፥42፤ ሉቃ6፥34፤ ሐሥ24፥17
15፥9 ቍ፡1፤ ዘፀ22፥23፤ኢዮ5፥15፤ ማቴ20፥15፤ያዕ5፥4
15፥10 2ቆሮ9፥5፤ ዘዳ14፥29
15፥11 ቍ፡7፤ ማቴ26፥11፤ ማር14፥7፤ዮሐ12፥8
15፥12 ኤር34፥14
15፥14 ዘኍ18፥27
15፥15 ዘፀ13፥3፤ 20፥2፤ ዘዳ4፥34፤ 9፥26፤16፥12፤24፥18፤ ኤር16፥14፤23፥7፤ 34፥13፤
15፥19 ዘፍ4፥4፤ ዘፀ13፥2፤22፥30፤ ዘሌ27፥9
15፥20 ዘሌ7፥15-18፤ ዘዳ12፥5-7፡17፡18
15፥21 ዘፀ12፥5፤ ዘሌ22፥19-25፤ ዘዳ17፥1፤ሚል1፥8፡13
15፥22 ዘዳ12፥15
15፥23 ዘፍ9፥4፤ ዘዳ12፥16፤ሕዝ33፥25
16፥1 ዘፀ12፥2፡11፤ 2ነገ23፥21፤ ማቴ26፥17-29
16፥2 ዘዳ12፥5፡26

15፥4 *በመካከልህ ድኻ አይኖርም፤* በመካከላቸው ድኻ የማይኖረው፣ እግዚአብሔር እርሱን ለሚታዘዙ ሁሉ በረከቱን ስለሚሰጥና (ቍ 4-6) በሰባተኛው ዓመት ድኾች ሁሉ ነጻ ስለሚወጡ ነው (ቍ 7-11)። ይህ “ዕዳ የሚተውበት ዓመት” (ቍ 9) የኑሮ ችግር ለገጠማቸው እስራኤላውያን ከዕዳ ነጻ የመሆን ዕድል የሚሰጣቸው ሲሆን፣ አልፎ ተርፎም በማኅበረሰቡ ውስጥ የሀብት መበላለጥ እንዳይኖር ያደርጋል። ‘ኢዮቤልዩ ዓመት’ የሚያስገኘውን ጥቅም ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (ዘሌ 25፥8-38)።

15፥6 *ታበድራለህ፤* እስራኤላውያን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ካልጠበቁ ማበደር ቀርቶ የሚበደሩ ይሆናሉ (28፥43-44 *ይመ*)።

15፥11 *ድኾች ምን ጊዜም አይጠፉም፤* ኢየሱስ በማቴ 26፥11 ላይ የተናገረውን ይመ። መልካም ሕግ አላቸው በሚባሉት ኅብረተሰቦች ውስጥ እንኳ፣ የኑሮ ዋስትና አለመኖርና የገቢ ሁኔታ አለመመጣጠን፣ በኅብረተ ሰብ ውስጥ ድኾች እንዲኖሩ ያደርጋል። እንዲህ ባለው ጊዜ ለድኾችና ለችግረኞች የልግስናንና የርኅራኄን እጅ እንድንዘረጋ ጌታ አዞአል።

15፥15 *አስታውስ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

15፥16 *አንተንና ... ከመውደዱ፤* በዘፀ 21፥5-6 ላይ አገልጋዩ መሄድ ካልፈለገ ከቤተ ሰቡ ጋር መኖር ይችላል የሚል ተጨማሪ ምክንያት ተሰጥቶአል።

15፥17 *ጆሮውን ... በወስፌ ትበሳዋለህ፤* የዘፀ 21፥6 ማብ ይመ።

15፥18 *ዕጥፍ፤* አንድ ዕብራዊ አገልጋይ የሐሙራቢ ሕግ ከዕዳ ነጻ ለመውጣት ከሚጠይቀው በላይ፣ ዕጥፍ ዓመታትን እንዲያገለግል ይጠበቅበታል። “ስድስት ዓመት” በሚለው ፈንታ የሐሙራቢ ሕግ “ሦስት ዓመት” ይላል። ሌሎች ጥንታዊ የሕግ ሰነዶች፣ “ዕጥፍ” በሚለው ቃል ፈንታ፣ “አቻ ወይም እኩል” ይላሉ።

15፥19 *ተባዕት በኵር ሁሉ ... ቀድስ፤* ወንድ የሆነ በኵር ሁሉ ለእግዚአብሔር የተለየ እንዲሆን የተደረገው፣ እግዚአብሔር መቅሠፍቱን በግብፃውያን ላይ ባወረደ ጊዜ ሕዝቡን ከዚህ መቅሠፍት ስላዳነ ነው (ዘፀ 12፥12፡29፤ 13፥2 እና ማብ እንዲሁም 13፥15 *ይመ*)።

15፥21 *አንድ እንስሳ እንከን ካለበት ... አትሠዋው፤* የዘሌ 1፥3 ማብ ይመ።

*15፥23፤* 12፥16፡24 እንዲሁም የዘፍ 9፥4፤ የዘሌ 17፥11 ማብ ይመ።

*16፥1-17፤* በገጽ 178 ላይ፣ “የብሉይ ኪዳን በዓላትና ሌሎች የተቀደሱ ቀናት” የሚለውን ሠንጠረዥ ይመ። እንዲሁም ዘፀ 23፥14-19 እና ማብ፤ 34፥18-26፤ ዘሌ 23፥4-44 ማብ፤ ዘኍ 28፥16-29፡40 ይመ።

*16፥1-8፤* ዘፀ 12፥1-28፤ 13፥1-16 እና ማብ ይመ።

16፥1 *አቢብ፤* በገጽ 101 ላይ፣ “የዕብራውያን የቀን አቈጣጠር” የሚለውን ሠንጠረዥ ይመ።

እንስሳ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፋሲካ አድርገህ ሠዋው። [3]ከቦካ ቂጣ ጋር አትብላው፤ ከግብፅ የወጣኸው በችኮላ ነውና ከግብፅ የወጣህበትን ጊዜ በሕይወትህ ዘመን ሁሉ ታስብ ዘንድ የመከራ ቂጣ ሰባት ቀን ብላ። [4]በምድርህ ሁሉ ላይ በአንተ ዘንድ ለሰ ባት ቀን እርሾ አይገኝ፤ በመጀመሪያው ዕለት ምሽት ከምትሠዋውም ላይ ማናቸውንም ሥጋ ሧት ድረስ እንዲቈይ አታድርግ።

[5]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ በማናቸውም ከተማ ፋሲካን መሠዋት አይገባህም፤ [6]ነገር ግን ለስሙ ማደሪያ ይሆን ዘንድ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚመርጠው ስፍራ፣ ፀሓይ ስትጠልቅ ምሽቱ[ж] ላይ ከግብፅ በወጣህበት ሰዓት ዓመታዊ መታሰቢያ (በዚያ) ፋሲካን ሠዋ። [7]ሥጋውንም ጠብሰህ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚመርጠው ስፍራ ብላ፤ ሲነጋም ወደ ድንኳንህ ተመልሰህ ሂድ። [8]ስድስት ቀን ያልቦካ ቂጣ ብላ፤ በሰባተኛው ቀን *ለአም ላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የተቀደሰ ጉባኤ አድርግ፤ ሥራም አትሥራበት።

## የመከር በዓል

16፥19-12 ተጓ ምብ - ዘሌ 23፥15- 22፤ ዘኍ 28፥26- 31

[9]እህልህን ማጨድ ከምትጀምርበት ዕለት አንሥቶ ሰባት ሳምንት ቍጠር፤ [10]ከዚያም በኋላ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በባረከህ መጠን፣ በፈቃድህ የምታመጣውን ስጦታ በማ ቅረብ የመከሩን በዓል *አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) አክብር። [11]አንተ፣ ወንዶችና ሴቶች ልጆችህ፣ ወንዶችና ሴቶች አገልጋዮችህ፣ በከተሞችህ ያለ ሌዋዊና መጻተኛ በመካከልህ የሚኖሩ አባት የሌላቸውና መበለቶች *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለስሙ ማደሪያ እንዲሆን በሚመርጠው ስፍራ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ደስ ይበላችሁ። [12]አንተም በግ ብፅ ባሪያ እንደነበርህ አስታውስ፤ ይህንንም በጥንቃቄ ጠብቅ።

## የዳስ በዓል

16፥13-17 ተጓ ምብ ዘሌ 23፥33-43 ዘኍ 29፥12-39

[13]የእህልህን ምርት ከዐውድማህ፣ ወይንህንም ከመጭመቂያህ ከሰበሰብህ በኋላ፣ የዳስን በዓል ሰባት ቀን አክብር። [14]በበዓልህ አንተ፣ ወንድና ሴት ልጅህ፣ ወንድና ሴት አገልጋይህ፣ በከተ ማው ያለሌዋዊ፣ መጻተኛ፣ አባት አልባውና መበለቲቱ ደስ ይበላችሁ። [15]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በመረጠው ስፍራ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በዓሉን ሰባት ቀን አክብር፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእህል ምርትህና በእጅህ ሥራ ሁሉ ይባርክሃል፤ ደስታህም ፍጹም ይሆናል።

[16]ወንዶችህ ሁሉ በዓመት ሦስት ጊዜ፣ በቂጣ በዓል፣ በመከር በዓልና በዳስ በዓል ላይ፣ እርሱ በሚመርጠው ስፍራ *በአምላክህ* በእግዚ አብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ይቅረቡ፤ ማንም ሰው *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ባዶ እጁን አይቅ ረብ። [17]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በባረከህ መጠን እያንዳንዱ እንደ ችሎታው ይስጥ።

## ስለ ፍርድ አሰጣጥ

[18]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ ከተሞች ሁሉ ለየነገዶችህ ዳኞችንና አለቆችን ሹም፤ እነርሱም ሕዝቡን በቅን ፍርድ ይዳኙ። [19]ፍርድ አታዛባ፤ አድልዎ አታድርግ፤ ጉቦም አትቀበል፤ ጉቦ የጠቢባንን ዐይን ያሳውራል፤ የጻድቃንንም ቃል ያጣምማልና። [20]በሕይወት እንድትኖርና *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚሰጥህን ምድር እንድትወርስ፣ ቅን ፍርድን ብቻ ተከተል።

## ሌሎችን አማልክት ስለ ማምለክ

[21]*ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በምት ሠራው መሠዊያ አጠገብ የአሼራን ምስል የዕንጨት ዐምድ አታቁም[፣]። [22]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚጠላውን ማምለኪያ ዐምድ ለአንተ አታቁም።

**17** እንከን ወይም ጕድለት ያለበትን በሬ ወይም በግ በእርሱ ዘንድ አስጸያፊ ነውና *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አት ሠዋ።

[2]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሚሰጥህ ከተሞች በአ ንዲቱ አብሮህ የሚኖር ወንድ ወይም ሴት ኪዳኑን በማፍረስ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ክፉ ድርጊት ሲፈጽም ቢገኝ፣ [3]ትእዛዜንም በመተላለፍ ባዕዳን አማልክትን ያመለከ፣ ለእርሱም ማለትም ለፀሓይ ወይም ለጨረቃ ወይም ለሰማይ ከዋክብት የሰገደ፣ [4]አንተም ይህ መደረጉን ብትሰማ፣ ነገሩን በጥንቃቄ መርምር፤ የተባለውም እውነት ከሆነና እንዲህ ያለው አስጸያፊ ነገር በእስ ራኤል ዘንድ መፈጸሙ ከተረጋገጠ፣ [5]ይህን

16፥3 ዘፀ12፥8፡ 11:39፥34፥18፤ ዘዳ4፥9፤1ቆሮ5፥8፤
16፥4 ዘፀ12፥6:8፤ ማር14፥12
16፥6 ዘፀ12፥42
16፥7 ዘፀ12፥8
16፥8 ዘሌ23፥8፤ ማቴ26፥17፤ ሉቃ2፥41፤22፥7፤ ዮሐ2፥13
16፥9 ዘፀ23፥16፤ ሐሥ2፥1
16፥11 ዘፀ20፥24፤ ዘዳ12፥7፤ዘዳ12፥12፤ 14፥29፤2ሳሙ7፥13፤ ነህ8፥10
16፥12 ዘዳ15፥15
16፥13 ዘኖ27፥37፤ ዘፀ23፥16ዘሌ2፥14፤
16፥14 ቀኍ11
16፥15 ኢዩ38፥7፤ መዝ4፥7፤28፥7፤30፥11
16፥16 ዘፀ12፥17፤ 23፥14:16፤34፥20፤ ዘዳ31፥11፤መዝ84፥7፤ ዕዝ3፥4
16፥18 ዘኖ31፥37፤ ዘፀ18፥21:26፤
16፥19 ዘፀ18፥21፤ 23፥2፤ዘሌ19፥15፤ 1ሳሙ8፥3
16፥21 ዘፀ34፥13፤ ዘዳ7፥5፤1ነገ14፥15፤ 2ነገ17፥16፤21፥3፤ 2ዜና33፥3
16፥22 ዘፀ23፥24
17፥1 ዘፀ12፥5፤ ዘሌ22፥20፤ዘዳ7፥25፤ 15፥21
17፥2 ዘዳ13፥6-11
17፥3 ዘኖ1፥16፤ 2፥1፤37፥9፤ዘፀ22፥20፤ ኤር7፥31
17፥4 ዘዳ22፥20፤ 13፥12-14
17፥5 ዘሌ24፥14

[ж]6 ወይም፣ *ፀሓይ ስትወጣ ንጋቱ ላይ፡*
[፣]21 ወይም፣ *ለአሼራ ብለህ ምንም ዐይነት ዛፍ አትትከል።*

16፥3:12 *ታስብ ዘንድ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።
16፥6 *ዓመታዊ መታሰቢያ፤* ከዚህ ቀደም ሲል ያሉት ሐረጎች እንደሚያመለክቱት የቀኑን ጊዜ ወይም ከግብፅ ለቀው የወጡበትን ዕለት ሊያመለክት ይችላል።
16፥7 *ወደ ድንኳንህ፤* በዓሉን ካከበራችሁ በኋላ ወዳረፋችሁበት ቤት ተመለሱ ማለት ነው፤ ይህም በቋሚነት ወይም በጊዜያዊነት የሚኖሩበት ሊሆን ይችላል።
16፥8 *ጉባኤ፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ፣ "የመዝጊያ ጉባኤ" የሚል ትርጒም ሳይኖረው አይቀርም፤ ዘሌ 23፥36 ይመ።
16፥9 *እህልህን ማጨድ ከምትጀምርበት ዕለት አንሥቶ፤* በአቢብ ወር በ16ኛው ቀን ማለት ነው፤ ይህም የፋሲካ በዓል የሚከበርበት ሁለተኛው ቀን ነው።
16፥15 *ደስታህም ፍጹም ይሆናል፤* ደስታቸው ፍጹም የሚሆነው ከእግዚአብሔር በረከት የተነሣ ነው (ከዮሐ 3፥29፤15፥11፤ 16፥24፤ ከፊል 2፥2፤ ከ1ዮሐ 1፥4፤ ከ2ዮሐ 12ጋር ያነጻጽሩ)።
16፥16 *በዓመት ሦስት ጊዜ፤* ሦስቱን ዓመታዊ ክብረ በዓላት ሲሆን፣ እነዚህን ሦስት ታላላቅ በዓላት ለማክበር ወደ ተመረጠው ማእከላዊ ስፍራ መሄድ ያስፈልግ ነበር (ዘፀ 23፥14:17፤ 34፥23 ይመ)።
16፥17 *በባረከህ መጠን እያንዳንዱ እንደችሎታው ይስጥ፤* ቍ 10 ይመ፤ ከ2ቆሮ 8፥12 ጋር ያነጻጽሩ።
*16፥18-20፤* ከ1፥9-18፤ ከዘፀ 18፥13-26 ጋር ያነጻጽሩ።
*16፥19፤* ዘፀ 23፥8 እና ማብ ይመ።
16፥21-22 *የአሼራን ምስል የዕንጨት ዐምድ ... ማምለኪያ ዐምድ፤* የ7፥5 ማብ ይመ።
17፥1 *እንከን ወይም ጕድለት፤* የዘሌ 1፥3 ማብ ይመ።
17፥3 *ለፀሓይ ወይም ለጨረቃ ወይም ለሰማይ ከዋክብት የሰገደ፤* 2ነገ 17፥16፤ 21፥3:5፤ 23፥4-5 ይመ።

ክፉ ድርጊት የፈጸመውን ወንድ ወይም ሴት ወደ ከተማ ደጅ ወስደህ፣ ያን ሰው እስኪ ሞት ድረስ በድንጋይ ውገረው:: [6]ሞት የሚ ገባው ሰው፣ በሁለት ወይም በሦስት ሰዎች ምስክርነት ይገደል፤ ነገር ግን በአንድ ሰው ምስክርነት ብቻ ማንም ሰው አይገደል:: [7]ሲገ ደልም መጀመሪያ የምስክሮቹ እጅ፣ ቀጥ ሎም የሕዝቡ ሁሉ እጅ ይረፍበት፤ ክፉን ከመካከልህ አስወግድ::

## የፍርድ አደባባይ

[8]በአንድ የነፍስ ግድያ ዐይነትና በሌላ፣ በአንድ ዐይነት ሕጋዊ ክርክርና በሌላ፣ ወይም በአንድ የክስ ዐይነትና በሌላ መካከል ውሳኔ የሚጠ ይቅ ማንኛውም ጉዳይ ቢነሣ፣ ከዐቅምህ በላይ የሆነ ጉዳይ በከተሞችህ ውስጥ ቢያጋጥምህ፣ ተነሥተህ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚመርጠው ስፍራ ውጣ፤ [9]ካህናት ወደ ሆኑት ሌዋውያንና በዚያን ጊዜ ዳኛ ወደ ሆነው ሰው ሂደህ፣ ስለ ጉዳዩ ጠይቃቸው፤ እነር ሱም ውሳኔውን ይነግሩሃል:: [10]አንተም *እግዚ አብሔር* (ያህዌ) በሚመርጠው ስፍራ እነርሱ በሚሰጡህ ውሳኔ መሠረት ፈጽም፤ እንድትፈ ጽም የሚሰጡህን መመሪያ ሁሉ በጥንቃቄ አድርግ:: [11]በሚያስተምሩህ ሕግና በሚሰጡህ መመሪያዎች መሠረት ፈጽም:: እነርሱ ከሚነ ግሩህ ቀኝም ግራም አትበል:: [12]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ለማገልገል በዚያ የሚቆመውን ካህን ወይም ዳኛ የሚንቅ ይገ ደል፤ ከእስራኤልም መካከል ክፉውን አስወግድ:: [13]ሕዝቡም ሁሉ ይህን ሲሰማ ይፈራል፤ ከዚያ ወዲያም እንዲህ ያለውን የንቀት ድርጊት አይደግመውም::

## ንጉሥን ስለማንገሥ

[14]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጥህ ምድር ስትገባ፣ በምትወርሳትና በምትቀመ ጥባት ምድር፣ "በዙሪያዬ እንዳሉት አሕዛብ ሁሉ፣ እኔም በላዬ ንጉሥ ላንግሥ" ብትል፣ [15]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚመ ርጠውን ንጉሥ በላይህ ታነግሣለህ፤ ከገዛ ወንድሞችህ መካከል እንጂ፣ እስራኤላዊ ወንድ ምህ ያልሆነውን ባዕድ በላይህ አታንግሥ:: [16]ንጉሡም ብዙ ፈረሶችን ለራሱ አያብዛ፤ ወይም ደግሞ የፈረሰኞችን ቍጥር ለመጨመር ሕዝቡን ወደ ግብፅ አይመልስ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ)፣ "በዚያ መንገድ ፈጽሞ አትመለሱ" ብሎአችኋልና:: [17]ልቡ እንዳይስትም ብዙ ሚስ ቶችን አያግባ፤ ብዙ ብርና ወርቅም አያግበ ስብስ::

[18]በመንግሥቱ ዙፋን ላይ በሚቀመጥበትም ጊዜ የዚህን ሕግ ቅጅ ከሌዋውያን ካህናት ወስዶ በጥቅልል መጽሐፍ ለራሱ ይጻፍ:: [19]*አምላኩን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ማክበር ይማር ዘንድ፣ የዚህን ሕግ ቃል ሁሉና ይህን ሥርዐት በጥንቃቄ ይከተል ዘንድ ከእርሱ ጋር ይሁን፤ በሕይወቱ ዘመን ሁሉ ያንብበው፤ [20]እርሱና ዘሮቹ በእስራኤል ላይ ረጅም ዘመን ይገዙ ዘንድ፣ ከሕጉ ቀኝም ግራም አይበል፤ ራሱን ከሌሎች ወንድሞቹ በላይ የተሻለ አድርጎ አይቍጠር::

## የካህናትና የሌዋውያን የመባ ድርሻ

18 ሌዋውያን ካህናት፣ የሌዊ ነገድም ሁሉ ከእስራኤል ጋር የመሬት ድርሻ ወይም ርስት አይኖራቸውም፤ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) በእሳት ከሚቀርበው መባ ይብሉ፣ ድርሻቸው ነውና:: [2]በወንድሞቻቸው መካከል ርስት አይኖራቸውም፤ በሰጣቸው ተስፋ መሠረት *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ርስታቸው ነው::

[3]ኰርማ ወይም በግ የሚሠዋው ሕዝብ ለካህኑ የሚሰጠው ድርሻ ወርቹን፣ መንገጭላ ውንና ሆድ ዕቃውን ነው:: [4]የእህልህን፣ የአዲሱን ወይንህንና የዘይትህን በኵራት እንዲ ሁም ከበጎችህ በመጀመሪያ የተሸለተውን ጠጕር ትሰጣለህ፤ [5]*በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ስም ቆሞ ለዘላለም ያገለግል ዘንድ *አምላክህ* እግ

17፥6 ዘኍ35፥30፤ ዘዳ19፥15፤ ማቴ18፥16
17፥7 ዘሌ24፥14፤ ዘዳ13፥5፤ሐሥ7፥58፤ ዮሐ8፥7፤1ቆሮ5፥13
17፥8 ዘፀ21፥6፤ ዘዳ12፥5፤2ዜና19፥10፤ መዝ122፥3-5
17፥9 ዘፍ25፥22፤ ዘፀ21፥6፤ዘዳ19፥17፤ 24፥8፤27፥9፤ ሕዝ44፥24፤ሐጌ2፥11
17፥11 ዘሌ10፥11፤ ዘዳ5፥32
17፥12 ቍ13፤ ዘፍ17፥14፤ዘኍ15፥30፤ 16፥9፤ዘዳ13፥5፡11፤ 18፥20፤19፥20፤ 1ነገ18፥40፤ኤር14፥14፤ ሆሴ4፥4፤ዘካ13፥3
17፥13 ቍ12
17፥14 ዘኍ33፥53፤ ኢያ21፥43፤ 1ሳሙ8፥5፡19-20፤ 10፥19
17፥15 1ሳሙ16፥3፤ 2ሳሙ5፥3፤ ኤር30፥21
17፥16 ዘፀ13፥17፤ 1ሳሙ8፥11፤1ነገ4፥26፤ 9፥19፤10፥26፡28፡29፤2ዜና1፥14፤መዝ20፥7፤ ኢሳ2፥7፤30፥16፤ 31፥1፤ኤር42፥14፤ ሕዝ17፥15፤
17፥17 ዘፀ34፥16፤ 2ሳሙ5፥13፤12፥11፤ 1ነገ10፥27፤11፥2፡3፤ 2ዜና1፥11፤11፥21፤ ምሳ31፥3፤ኢሳ2፥7
17፥18 ዘዳ31፥22፡ 24፤ኢያ24፥26፤ 1ሳሙ10፥25፤ 1ነገ1፥46፤1ዜና29፥23፤ 2ዜና23፥11
17፥19 ዘዳ4፥9-10፤ 11፥13፤ኢያ1፥8፤ 1ነገ3፥3፤11፥38፤ 2ነገ22፥2
17፥20 ዘዳ5፥32፤ ኢያ23፥6፡12፤ 1ሳሙ8፥5፤10፥25፤ 1ነገ2፥3፤ 9፥4፤1ዜና28፥8፤ መዝ119፥102
18፥1 ዘኍ18፥8፡20፤ ኤር33፥18፡21፤1ቆሮ9፥13
18፥2 ዘኍ18፥20፤ ኢያ13፥14
18፥3 ዘፀ29፥27፤ዘሌ1፥5፤ 7፥28-34፤ ዘኍ18፥12
18፥4 ዘፀ22፥29፤ ዘኍ18፥12
18፥5 ዘፀ28፥1፤ 29፥9፤ዘዳ10፥8

17፥6 *በሁለት ወይም በሦስት ሰዎች ምስክርነት፤* በዘኍ 35፥30 ላይ ይህን በተመለከተ ተጨማሪ ማብራሪያ ተሰጥቶአል:: 19፥15 ይመ፤ ከማቴ 18፥16፤ ከ2ቆሮ 13፥1፤ ከ1ጢሞ 5፥19፤ ከዕብ 10፥28 ጋር ያነጻጽሩ::

17፥7 *ክፉውንም ከመካከልህ ማስወገድ አለብህ፤* ቍ 12 ይመ፤ እንዲሁም የ13፥5 ማብ ይመ::

17፥14 *በዙሪያዬ እንዳሉት አሕዛብ ሁሉ ... ንጉሥ፤* ሙሴና ኢያሱ እንዲሁም ከእነርሱም በኋላ የተነሡት መሳፍንት በእግዚአብሔር ምትክ ሆነው እስራኤልን እንዲያስተዳድሩ የተመረጡት በራሱ በእግዚ አብሔር ነው:: በኋላም ጌዴዎን፣ "እግዚአብሔር ይገዛችኋል" እንዳለው ማለት ነው (መሳ 8፥23 እና ማብ ይመ):: ይሁን እንጂ፣ ሙሴ እዚህ ላይ ሕዝቡ፣ እግዚአብሔር ከሰጣቸው ሥርዐት በማፈንገጥ ወደ ፊት ንጉሥ ይንገሥልን ብለው እንደሚጠይቁ ተናግሮአል (1ሳሙ 8፥4-9 ይመ፤ እንዲሁም የ7፥2-5፤ የ1ሳሙ 8፥1-12፥25 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዘሌ 20፥23 ይመ):: ስለዚህ ሙሴ ወደ ፊት ንጉሥ እንዴት መምረጥ እንዳለባቸው መመሪያ ሰጣቸው::

17፥16-17፤ እስራኤልን ወደ ግብፅ የመለሰ መሪ አይኑር እንጂ (ኤር 42፥13-43፥7 ይመ)፣ የኋላ ኋላ በእስራኤል ላይ የነገሡ ነገሥታት፣ በተለይም ከንጉሥ ሰሎሞን ጀምሮ በዚህ ክፍል የተጠቀሱትን ነገሮች ሁሉ ተላልፈው ተገኝተዋል (1ነገ 4፥26፤ 11፥1-4)::

17፥18 *የዚህን ሕግ ቅጅ ... ለራሱ ይጻፍ፤* አንድ ንጉሥ የእግዚአብሔርን ሕግ ቅጅ ለራሱ የሚያስቀረው፣ እግዚአብሔር የእርሱ ንጉሥ እንደ መሆኑ ለእርሱ ብቻ መገዛት እንዳለበት ለማ ሳየትና በሰማይ የሚኖረውን ገዥ የሚታዘዘው በሕጉ ቃል መሠረት መሆኑን ለማመልከት ነው:: በዚህ ዘመንም ሆነ ከዚህ ዘመን በፊት በሒታውያንና በሌሎችም አገሮች ዘንድ፣ ከአንድ ንጉሥ በታች ሆነው የሚያስተዳድሩ ገዥዎች ይህን ሥርዐት የመከተል ግዴታ ነበረባቸው (የ31፥9 ማብ ይመ):: በገጽ 18 ላይ፣ "በብሉይ ኪዳን የተደረጉ ዋና ዋና ኪዳኖች" በሚል የተጻፈውን ሠንጠረዥ ይመልከቱ::

17፥20 *ራሱን ... የተሻለ አድርጎ አይቍጠር፤* ከእርሱ በታች ያሉ ሰዎች ሁሉ፣ ከሕግ በላይ እንዳልሆኑ ሁሉ፣ ንጉሡም ከእግዚአብሔር ሕግ በላይ ሊሆን አይችልም::

18፥1 *ድርሻ ወይም ርስት አይኖራቸውም፤* የግል የመሬት ይዞታ እንዲኖራቸው አልተፈቀደላቸውም:: ከሕዝቡ የሚሰበሰበው ዐሥራትና ለመሥዋዕት ከሚቀርቡት እንስሳት የተወሰነው ክፍል ለሌዋውያን እንደሚሰጥ ሁሉ (14፥22-29 እና ማብ እንዲሁም የዘሌ 27፥30 ማብ እና ዘኍ 18፥21-29 ይመ) ከተሞችና በአካባቢያቸው የሚገኙ የግጦሽ ቦታዎችም ለሌዋውያን ተለይተዋል (ኢያ 21፥41-42)::

18፥4 *በኵራት፤* ዘፀ 23፥19 እና ማብ፤ 34፥26፤ ዘሌ 23፥10-11፤ ዘኍ 15፥18-20፤ 18፥12-13 ይመ::

*18፥5፤* የ21፥5 ማብ ይመ::

እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከነገዶችህ ሁሉ እርሱንና ዘሮቹን መርጦአል::

[6]አንድ ሌዋዊ ከሚኖርበት ከየትኛውም በእስራኤል ካሉት ከተሞችህ መካከል በፍ ጹም ፈቃድ እግዚአብሔር (ያህዌ) ወደሚመ ርጠው ስፍራ ቢመጣ፣ [7]በእግዚአብሔር (ያህዌ) ፊት ቆመው እንደሚያገለግሉት ሌዋውያን ወንድሞቹ፣ እርሱም በአምላኩ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ስም ያገልግል:: [8]ከቤተ ሰቡ ንብ ረት ሽያጭ ላይ ገንዘብ ቢቀበል እንኳ፣ ባልንጀ ሮቹ ከሚያገኙት ጥቅም እኩል ይካፈላል::

## አስጸያፊ ድርጊቶች

[9]አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጥህ ምድር በምትገባበት ጊዜ፣ በዚያ የሚኖሩት አሕዛብ የሚፈጽሙትን አስጸያፊ መንገድ አትከተል:: [10]በመካከልህ ወንድ ወይም ሴት ልጁን በእሳት የሚሠዋ[x] ማርተኛ፣ ወይም መተተኛ፣ ሞራ ገላጭ፣ ጠንቋይ [11]ወይም በድግምት የሚጠነቍል፣ መናፍስት ጠሪ ወይም ሙት አነጋጋሪ በመካከልህ ከቶ አይገኝ:: [12]እነዚህን የሚያደርግ ሁሉ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ዘንድ አስጸያፊ ነውና፣ ከእነዚህ አጸያፊ ልምዶች የተነሣም አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እነዚያን አሕዛብ ከፊትህ ያባርራቸዋል:: [13]በአምላክህ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ነውር አልባ ሁን::

## ነቢይ ስለ መነሣቱ

[14]ምድራቸውን የምታስለቅቃቸው አሕዛብ፣ መተተኞችን ወይም ማርተኞችን ያዳምጣሉ፤ አንተ ግን ይህን እንድታደርግ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አልፈቀደልህም:: [15]አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከገዛ ወንድሞችህ መካከል እንደ እኔ ያለ ነቢይ ያስነሣልሃል፤ እርሱን አድምጥ:: [16]በኮሬብ ጉባኤ በተደረገበት ዕለት፣ "እንዳልሞት የአምላክህ የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ድምፅ አልስማ፤ እንዲህ ያለውንም አስፈሪ እሳት ደግሜ አልይ" ብለህ አምላክህን እግ ዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) የጠየቅኸው ይህን ነውና::

[17]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንዲህ አለኝ፤ 'የተናገሩት መልካም ነው፤ [18]ከወንድሞቻቸው መካከል እንደ አንተ ያለ ነቢይ አስነሣላቸዋለሁ፤ ቃሌን በአፉ አደርጋለሁ፤ የማዘውንም ሁሉ ይነግራ ቸዋል:: [19]ማንም ሰው ነቢዩ በስሜ የሚናገረ ውን ቃሌን ባይሰማ፣ እኔ ራሴ በተጠያቂነት እይዘዋለሁ:: [20]ነገር ግን እንዲናገር እኔ ያላዘዝ ሁትን ቃል በድፍረት በስሜ የሚናገርም ሆነ በሌሎች አማልክት ስም የሚናገር ነቢይ ይገ ደል::"

[21]አንተም በልብህ፣ "ከእግዚአብሔር (ያህዌ) ያልተነገረውን መልእክት እንዴት ማወቅ እንችላለን?" ብትል፣ [22]ነቢዩ በእግዚአብሔር (ያህዌ) ስም የተናገረው ካልተፈጸመ ወይም እውነት ሆኖ ካልተገኘ፣ መልእክቱ እግዚ አብሔር (ያህዌ) የተናገረው አይደለም:: ያ ነቢይ በድፍረት ተናግሮታልና እርሱን አትፍራው::

## መማጸኛ ከተሞች

19፥1–14 ማመ – ዘኍ 35፥6-34፤ ዘዳ 441-43፤ ኢሱ 2፥1-9

**19** አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ምድ ራቸውን ለአንተ የሚሰጥባቸውን አሕዛብ በሚደመስሳቸው ጊዜና አንተም እነርሱን አስለ ቅቀህ በከተሞቻቸውና በቤቶቻቸው በምትቀመ ጥበት ጊዜ፣ [2]አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድር አማካይ ስፍራ፣ ሦስት ከተሞችን ለራስህ ለይ:: [3]ሰው የገደለ ሁሉ እንዲሸሸባቸው አምላክህ እግዚአ ብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድር መንገዶችን ሥርተህ፣ በሦስት ክፈላቸው::

[4]በተንኰል ሳይሆን ድንገት ሳያስበው ባል ንጀራውን ገድሎ ሕይወቱን ለማትረፍ ለሚሸሽ ሰው መመሪያው የሚከተለው ነው:: [5]እነሆ፤ አንድ ሰው ከባልንጀራው ጋር እንጨት ለመ ቍረጥ ወደ ጫካ ቢሄድ፣ ዛፉን ለመጣል መጥረቢያውን በሚሰነዝርበት ጊዜ ብረቱ ከእጀታው ወልቆ ባልንጀራውን በመምታት ቢገድለው፣ ያ ሰው ከእነዚህ ከተሞች ወደ አንዱ በመሸሽ ሕይወቱን ማትረፍ ይችላል:: [6]አለበለዚያ በተንኰል ሳይሆን ድንገት ሳያስ በው ባልንጀራውን ቢገድል፣ መንገዱ ረጅም ከሆነ ደም ተበቃዩ በንዴት ተከታትሎ ይደር ስበትና፣ መገደል የማይገባውን ሰው ሊገድል ይችላል:: [7]ሦስት ከተሞችን ለራስህ እንድትለይ ያዘዝሁህ በዚሁ ምክንያት ነው::

[8]ለአባቶችህ በመሐላ በገባላቸው ቃል መሠረት አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወሰንህን ሲያሰፋ

18፥6 ዘኍ35፥2-3፤ ዘዳ12፥5
18፥7 ቍ19፤ 1ነገ18፥32፤22፥16፤ መዝ118፥26
18፥8 ዘኍ18፥24፤ 2ዜና31፥4፤ነህ12፥44፡ 47፤13-12
18፥9 ዘሌ18፥3፤ ዘዳ9፥5፤12፥29-31፤ 2ነገ21፥2፤2ዜና28፥3፤ 33፥2፤34፥33፤ ዕዝ6፥21፤9፥11፤ ኤር44፥4
18፥10 ዘፀ7፥11፤ ዘሌ18፥21፤19፥31፤ 1ሳሙ15፥23
18፥11 ዘፀ22፥18፤ 1ሳሙ28፥13፤ ኢሳ47፥9
18፥12 ዘሌ18፥24
18፥13 ዘፍ6፥9፤ መዝ119፥1፤ማቴ5፥48
18፥14 2ነገ21፥6
18፥15 ማቴ21፥11፤ ሉቃ2፥25-35፤ ዮሐ1፥21፤ሐሥ3፥22፤ 7፥37
18፥16 ዘፀ20፥19፤ ዘዳ5፥23-27
18፥18 ዘፍ20፥7፤ ዘፀ4፥12፤ኢሳ2፥3፤ 26፥8፤51፥4፤ሚክ4፥2፤ ዮሐ4፥25-26፤ 14፥24፤ሐሥ3፥22
18፥19 ቍ7፤ ዘፀ23፥21፤ ዘሌ19፥12፤2ነገ2፥24፤ ኢሱ22፥23፤ ሐሥ3፥23፤ዕብ12፥25
18፥20 ዘፀ23፥13፤ ዘዳ13፥1-5፤17፥12
18፥22 ቍ20፤ ዘዳ13፥2፤1ሳሙ3፥20፤ 1ነገ22፥28፤ኤር28፥9
19፥1 ዘዳ6፥10-11
19፥6 ዘኍ35፥12
19፥8 ዘፍ15፥8፤ ዘፀ34፥24፤ዘዳ11፥24

[x]10 ወይም፣ *ወንድ ወይም ሴት ልጁን የሚገድል*::

18፥9 *አሕዛብ የሚፈጽሙትን አስጸያፊ መንገድ፤* ከዚህ ቀጥሎ የሚገኘው የአስማተኝነትንና የመናፍስት ጠሪነትን ተግባር አስመልክቶ፣ በብሉይ ኪዳን ከተሰጠው ዝርዝር ሁሉ እጅግ የተሟላ ዝርዝር ነው:: በዚህ ክፍል የተጠቀሱት ሁሉ በከነዓን ምድር የሚገኙ ዐጕል ልማዶች ሲሆኑ፣ ሁሉም በእግዚአብሔር ተወግዘዋል፤ ተከልክለዋል:: የእግዚአብሔር ሕዝብ መረጃን፣ ምሪትንና ራእይን ፍለጋ ወደ እነዚህ ሰዎች መሄድ የለበትም:: ከዚህ ይልቅ ግን የእግዚአብሔር እውነተኛ ነቢያት የሚያመጡለትን መልእክት ማድመጥ ይገባዋል (ቍ 14-22 ይመ)::

18፥10 *ወንድ ወይም ሴት ልጁን በእሳት የሚሠዋ፤* 12፥31 ይመ፤ እንዲሁም የዘሌ 18፥21 ማብ ይመ::

18፥15 *እንደ እኔ ያለ ነቢይ፤* ቍ 16 እንዲሁም የክፍሉ አጠ ቃላይ ዐውድ (በተለይ ቍ 20-22 ይመ) እንደሚያመለክተው፣ በየጊ ዜው የሚነሡ ነቢያትን ማለት ነው:: በኮሬብ ተራራ ላይ ሕዝቡ ሙሴ ከእግዚአብሔር መልእክት ተቀብሎ እንዲነግራቸው ጠይቀው ነበር (ዘፀ 20፥19 እና ማብ ይመ):: አሁን ግን ሙሴ ሊለያቸው በመሆኑ ሌላ የእግዚአብሔር ነቢይ የእርሱን ቦታ እንደሚተካና ወደፊት ለሚነሣው ትውልድ ደግሞ ሌላ ነቢይ እንደሚያስፈልግ ነገ ራቸው:: ስለዚህ፣ "እንደ እኔ ያለ ነቢይ" ሲል ከእርሱ በኋላ የሚነሡ ነቢያትን የሚያሳይ የወል አመልካች ነው:: ከዚህም በተጨማሪ ወደፊት የሚመጣውን መሲሕ የሚያመለክትና ልዩ በሆነ መንገድ በኢየሱስ የተፈጸመ ቃል ነው (ዮሐ 1፥21፡25፡45፤ 5፥46፤ 6፥14፤ 7፥40፤ ሐሥ 3፥22-26፤ 7፥37 ይመ)::

*18፥16፤* ዘፀ 20፥18-19፤ ዕብ 12፥18-21 ይመ::

18፥18 *ቃሌንም በአፉ፤* ዘፀ 4፥15-16፤ እንዲሁም የዘፀ 7፥1-2 ማብ ይመ::

18፥20 *በድፍረት ... የሚናገር ነቢይ፤* የ13፥1-5 ማብ ይመ:: *ይገደል፤* 13፥5፤ ኤር 28፥15-17 ይመ::

*18፥21-22፤* ይህ በአሉታዊ አነጋገር የቀረበው ዐረፍተ ነገር ሁልጊዜ እውነትነት አለው:: ሆኖም "የተነገረው ትንቢት ከተፈጸመ ከእግዚአብሔር ነው" ተብሎ በአዎንታዊ አነጋገር የቀረበ ዐረፍተ ነገር ሁልጊዜ እውነትነት ላይኖረው ይችላል (የ13፥1-5 ማብ ይመ)::

*19፥1-13፤* 4፥41-43፤ ዘኍ 35፥9-28፤ ኢሱ 20 ይመ::

ውና ለእነርሱ በሰጣቸው መሠረት ምድሪቷን ሁሉ ሲሰጥህ፣ 9*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትወድና ምንጊዜም በመንገዱ እንድትሄድ ዛሬ የማዝዝህን እነዚህን ሕግጋት ሁሉ በጥንቃቄ የምትጠብቅ ከሆነ፣ በእነዚህ ላይ ሌሎች ሦስት ከተሞችን ትጨምራለህ። 10*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድር የንጹሕ ሰው ደም እንዳይፈስና በሚፈሰውም ደም በደለኛ እንዳትሆን ይህን አድርግ።

11ይሁን እንጂ አንድ ሰው ባልንጀራውን ቢጠላው፣ አድፍጦ ጥቃት ቢያደርስበት፣ ቢገድለውና፣ ከእነዚህ ከተሞች ወደ አንዲቱ ቢሸሽ፣ 12የሚኖርባት ከተማ ሽማግሌዎች ሰው ልከው ከከተማው ያስመጡት፤ እንዲገድለውም ለደም ተበቃዩ አሳልፈው ይስጡት። 13አትራራለት፤ ነገር ግን መልካም እንዲሆንልህ የንጹሑን ደም በደል ከእስራኤል አስወግድ።

14*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትወርሳት በሚሰጥህ ምድር ውስጥ ለአንተ በሚተላለፍልህ ርስት ላይ የቀድሞ ሰዎች ያስቀመጡትን የባልጀራህን የድንበር ምልክት አታንሣ።

## ምስክሮች

15በማናቸውም ወንጀል ወይም ሕግ በመተላለፍ ሰውን ጥፋተኛ ለማድረግ፣ አንድ ምስክር አይበቃም፤ ጉዳዩ በሁለት ወይም በሦስት ሰዎች ምስክርነት መረጋገጥ አለበት።

16ተንኰለኛ የሆነ ምስክር አንድን ሰው በሐሰት ቢከስ፣ 17ክርክሩ የሚመለከታቸው ሁለቱ ሰዎች *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) *ፊት*፣ በዚያ ወቅት በሚያገለግሉት ካህናትና ፈራጆች ፊት ይቅረቡ። 18ፈራጆችም ጉዳዩን በጥልቅ ይመርምሩት፤ ያም ምስክሩ በወንድሙ ላይ በሐሰት የመሰከረ መሆኑ ከተረጋገጠ፣ 19በወንድሙ ላይ ለማድረግ ያሰበውን በእርሱ ላይ አድርግበት፤ ክፉውን ከመካከልህ አስወግድ። 20የቀሩትም ሰዎች ይህን ሰምተው ይፈራሉ፤ እንዲህ ያለው ክፉ ነገርም ለወደፊቱ በመካከልህ ከቶ አይደገምም። 21ርኅራኄ አታድርግ፤ ሕይወት በሕይወት፣ ዐይን በዐይን፣ ጥርስ በጥርስ፣ እጅ በእጅ፣ እግር በእግር ይመለስ።

## ለጦርነት መውጣት

**20** ጠላቶችህን ለመውጋት ወደ ጦርነት ስትሄድ፣ ሠረገሎችንና ፈረሶችን ከአንተ የሚበልጥ ሰራዊትንም በምታይበት ጊዜ አትፍራቸው፤ ከግብፅ ያወጣህ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከአንተ ጋር ነውና። 2ወደ ውጊያው ቦታ ስትቃረቡ፣ ካህኑ ወደ ፊት ወጣ ብሎ ለሰራዊቱ ይናገር፤ 3እንዲህም ይበል፤ "እስራኤል ሆይ ስማ፤ በዛሬው ቀን ጠላቶቻችሁን ለመግጠም ወደ ጦርነት ልትገቡ ነው፤ ልባችሁ አይባባ፤ አትፍሩ፤ አትደንግጡ፤ በጠላቶቻችሁ ፊት አትሸበሩ፤ 4ድልን ያቀዳጃችሁ ዘንድ ስለ እናንተ ጠላቶቻችሁን ሊወጋ አብሮአችሁ የሚወጣው *አምላካችሁ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ነውና።"

5አለቆቹም ለሰራዊቱ እንዲህ ይበሉ፤ "አዲስ ቤት ሠርቶ ያላስመረቀ አለን? ወደ ቤቱ ተመልሶ ይሂድ፤ ያለበለዚያ በጦርነቱ ላይ ይሞትና ቤቱን የሚያስመርቀው ሌላ ሰው ይሆናል። 6ወይን ተክሎ ገና ያልበላለት አለን? ወደ ቤቱ ይመለስ፤ ያለበለዚያ በጦርነቱ ላይ ይሞትና ወይኑን ሌላ ሰው ይበላዋል። 7ሚስት አጭቶ ያላገባት አለን? ወደ ቤቱ ይመለስ፤ ያለበለዚያ በጦርነቱ ይሞትና ሌላ ሰው ያገባታል።" 8ከዚያም አለቆቹ፣ "የሚፈራ ወይም ልቡ የሚባባ ሰው አለን? የወንድሞቹም ልብ እንዳይባባ ወደ ቤቱ ይመለስ" በማለት ጨምረው ይናገሩ።

9አለቆቹ ለሰራዊቱ ተናግረው ሲያበቁ፣ አዛዦችን በሰራዊቱ ላይ ይሹሙ።

10አንድን ከተማ ለመውጋት በምትዘምትበት ጊዜ፣ አስቀድመህ ለሕዝቧ የሰላም ጥሪ አስተላልፍ፤ 11ከተቀበሉህና ደጆቻቸውን ከከፈቱልህ በከተማዋ ውስጥ ሕዝብ ሁሉ ገባርህ ይሁን፤ ያገልግሉህም። 12ዕርቀ ሰላምን ባለመቀበል ውጊያን ከመረጡ፣ ከተማዪቱን ከበባት። 13*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አሳልፎ በእጅህ በሰጠህ ጊዜ፣ በውስጧ ያሉትን ወንዶች በሙሉ በሰይፍ ግደላቸው። 14ነገር ግን ሴቶቹን ሕፃናትን፣ እንስሳቱንና በከተማዪቱ ውስጥ የሚገኘውን ማናቸውንም ነገር በምርኮ ለራስህ አድርግ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከጠላቶችህ የሚሰጥህን ምርኮ ልትጠቀምበት ትችላለህ። 15እንግዲህ የአካባቢህ አሕዛብ ከተሞች ባልሆኑትና ከአንተ እጅግ ርቀው በሚገኙት ከተሞች ሁሉ ላይ የምታደርገው ይኸው ነው።

16*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጥህ በአሕዛብ ከተሞች ውስጥ፣

19፥9 ዘዳ6፥5
19፥10 ዘዳ21፥1-9፤ ምሳ6፥17፤ኤር7፥6፤ 26፥15
19፥11 ዘፀ21፥12፤ 1ዮሐ3፥15
19፥13 ዘዳ7፥2፤ 21፥9፤1ነገ2፥31
19፥14 ዘዳ27፥17፤ ኢዮ24፥2፤ ምሳ15፥25፤22፥28፤ 23፥10፤መዝ16፥6፤ ኢሳ1፥23፤ሆሴ5፥10
19፥15 ዘዳ17፥6፤ ማቴ18፥16፤26፥60፤ 2ቆሮ13፥1
19፥16 ዘፀ23፥1፤ ምሳ6፥19
19፥17 ዘፀ21፥6
19፥18 ዘፀ23፥7
19፥19 ምሳ19፥5፡ 9፤1ቆሮ5፥13
19፥20 ዘዳ13፥11
19፥21 ቊ13፤ ዘፀ21፥24፤ማቴ5፥38
20፥1 ዘኍ14፥9፤ ዘዳ3፥22፤1ሳሙ17፥45፤ መዝ20፥7፤ኢሳ31፥1፤ 41፥10
20፥3 1ሳሙ17፥32፤ ኢዮ23፥16፤መዝ22፥14፤ ኢሳ7፥4፤35፥4፤ ኤር51፥46
20፥4 ዘፀ14፥14፤ 1ዜና5፥22፤ 2ዜና20፥14-22፤ ነህ4፥20፤መሳ12፥3፤ 15፥18፤መዝ44፥7፤ 144፥10
20፥5 ነህ12፥27
20፥6 ኤር31፥5፤ ሕዝ28፥26፤ ሚክ1፥6፤1ቆሮ9፥7
20፥7 ዘዳ24፥5፤ ምሳ5፥18
20፥8 መሳ7፥3
20፥10 ዘዳ2፥26፤ ሉቃ14፥31-32
20፥11 ቊ15፤ 1ነገ9፥21፤2ነገ6፥22፤ 1ዜና22፥2፤ኢሳ31፥8
20፥13 ዘኍ31፥7
20፥14 ዘኍ31፥11፡ 53፤ኢያሱ8፥2፤22፥8
20፥15 ቊ11፤ ኢያሱ9፥9
20፥16 ዘፀ23፥31-33፤ ዘኍ21፥2-3፤ ዘዳ7፥2፤ኢያሱ6፥21፤

---

19፥14 *የድንበር ምልክት፤* በዚያን ዘመን የድንበር ምልክት የሚደረገው በድንጋይ ሲሆን፣ ምልክቶቹ የዕርሻ ቦታና የመሬት ይዞታ ክልል፣ ከየት እስከ የት እንደ ሆነ ያስታውቃሉ። የግል ይዞታን ለማስፋት የድንበር ምልክቶቹን ከቦታቸው ነቅሎ በሌላ ቦታ መትከል ትልቅ ወንጀል ነው።

*19፥15፤* የ17፥6 ማብ ይመ።

19፥18 *በሐሰት የመሰከረ፤* 5፥20፤ ዘሌ 19፥11-13፤ 1ነገ 21፥10:13 ይመ።

19፥19 *ክፉውን ከመካከልህ አስወግድ፤* የ13፥5 ማብ ይመ። ማብ ይመ 19፥21 *ሕይወት በሕይወት፤* የዘፀ 21፥24-25፤ ዘሌ 24፥20፤ እንዲሁም ማቴ 5፥38-42 ይመ።

20፥2 *ካህኑ ... ይናገር፤* ሥርዐቱን እየመላለሱ መናገር ማለት አይደለም። አንዳንድ ጊዜ ካህናት ሰራዊቱ ለጦርነት ሲወጣ አጅበው ይወጡ ነበር (ለምሳሌ ኢሱ 6፥4-21፤ 2ዜና 20፥14-22 ይመ)።

20፥3 *እስራኤል ሆይ ስማ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

*20፥4፤* የ3፥22 ማብ ይመ።

20፥5-8 *ወደ ቤቱ ተመልሶ ይሂድ፤* በ28፥30 ላይ የተጠቀሰውን ርግማን ይመ። እስራኤል መታመን ያለባት በሰራዊትዋ ብዛት ሳይሆን፣ በእግዚአብሔር ነው። ስለዚህም ከውትድርና ተግባር ነጻ የሚሆኑ ሰዎች ቍጥር አንዳንድ ጊዜ ብዙ ነበር (ለምሳሌ መሳ 7፥2-8)።

*20፥10-15፤* ይህ ክፍል በተስፋዪቱ ምድር ዙሪያ ከሚኖሩ ሕዝቦች ጋር ስለሚደረገው ጦርነት መመሪያን ይሰጣል።

20፥11 *ገባርህ ይሁን፤* የኖኅ ርግማን በልጁ በከነዓን ላይ መድረሱን ያሳያል (ዘፍ 9፥25 እና ማብ ይመ)።

እስትንፋስ ያለውን ነገር አታስተርፍ፤ [17]ኬጢያዊውን፣ አሞራዊውን፣ ከነዓናዊውን፣ ፌርዛዊውን፣ ኤዊያዊውን፣ ኢያቡሳዊውን *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባዘዘህ *መሠረት ፈጽመህ* ደምስሳቸው[ጀ]፤ [18]አለበለዚያ አማልክታቸውን በሚያመልኩበት ጊዜ የሚፈጽሟቸውን አስጸያፊ ተግባራት ሁሉ ታደርግ ዘንድ ያስተምሩሃል፤ *በአምላክህ* በእግዚአብሔርም (ያህዌ ኤሎሂም) ላይ ኀጢአት ትሠራለህ::

[19]አንድን ከተማ ተዋግተህ ለመያዝ የረጅም ጊዜ ከበባ ካደረግህ፣ ዛፎቹን በመጥረቢያ ጨፍጭፈህ አታጥፋ፤ የእነርሱን ፍሬ መብላት ትችላለህና አትቍረጣቸው፤ ከበህ የምታጠፋቸው የሜዳ ዛፎች ሰዎች ናቸውን?[1] [20]የሚበላ ፍሬ እንደማያፈራ የምታውቀውን ዛፍ ግን ልትቈርጠውና ጦርነት የምታካሄድባትን ከተማ በድል እስክትቈጣጠራት ድረስ ለከበባው ምሽግ *መሥሪያ* ልትጠቀምበት ትችላለህ::

## ገዳዩ ላልታወቀ ሰው ስለሚቀርብ ማስተስረያ

**21** *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትወርሳት በሚሰጥህ ምድር አንድ ሰው ተገድሎ ሜዳ ላይ ቢገኝና ገዳዩም ማን እንደ ሆነ ባይታወቅ፣ [2]ሽማግሌዎችህና ዳኞችህ ወጥተው ሬሳው ወድቆ ከተገኘበት አንሥቶ በአቅራቢያው እስካሉት ከተሞች ድረስ ያለውን ርቀት ይለኩ:: [3]ከዚያም ሬሳው ወድቆ ከተገኘበት ስፍራ በጣም ቅርብ የሆነችው ከተማ ሽማግሌዎች ሊሠራ ያልደረሰችና ቀንበር ያልተጫነባትን ጊደር ይዘው፣ [4]ከዚያ በፊት ታርሶ ወይም ተዘርቶበት ወደማይታወቅ ወራጅ ውሃ ወዳለበት ሸለቆ ያምጡት:: በዚያ ሸለቆም የጊደሪቱን ዐንገት ይስበሩ፤ [5]እንዲያገለግሉና *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ስም እንዲባርኩ፣ በማንኛውም የክርክርና የጥቃት ጕዳዮች ሁሉ ላይ ውሳኔ እንዲሰጡ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) መርጦአቸዋልና የሌዊ ልጆች ካህናቱ ወደ ፊት ይቅረቡ:: [6]ከዚያም ሬሳው በተገኘበት አቅራቢያ ባለችው ከተማ የሚኖሩ ሽማግሌዎች ሁሉ፣ በሸለቆው ውስጥ፣ ዐንገቷ በተሰበረው ጊደር ላይ እጃቸውን ይታጠቡ:: [7]እንዲህም ብለው ይናገሩ፤ "እጆቻችን ደም አላፈሰሱም፤ ድርጊቱ ሲፈጸምም ዐይኖቻችን አላዩም:: [8]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሆይ፤ ስለ ተቤዠኸው ሕዝብህ ስለ እስራኤል ብለህ ይህን ስርየት ተቀበል፤ ሕዝብህንም በፈሰሰው ንጹሕ ደም በደለኛ አታድርግ::" ስለ ፈሰሰውም ደም ስርየት ይደረግላቸዋል:: [9]አንተም *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ቀና የሆነውን ስታደርግ፣ የንጹሑን ደም የማፍሰስ በደልን ከመካከልህ ታስወግዳለህ::

## የተማረከች ሴት ስለ ማግባት

[10]ከጠላቶችህ ጋር ጦርነት ልትገጥም ወጥተህ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እነርሱን በእጅህ አሳልፎ ሰጥቶህ በማረክህ ጊዜ፣ [11]ከምርኮኞቹ መካከል መልከ መልካም ሴት አይተህ ብትማርክህ፣ ሚስትህ ልታደርጋት ትችላለህ:: [12]ወደ ቤትህ ውሰዳት፤ ጠጕሯን ትላጭ፤ ጥፍሯንም ትቍረጥ:: [13]ስትማረክ የለበሰችውንም ልብስ ታውልቅ፤ እቤትህ ተቀምጣ ለአባትና ለእናቷ ወር ሙሉ ካለቀሰችላቸው በኋላ፣ ልትደርስባትና ባል ልትሆናት፣ እርሷም ሚስት ልትሆንህ ትችላለች:: [14]በእርሷ ደስተኛ ባትሆን፣ ወደምትፈልገው እንድትሄድ ነጻነት ስጣት፤ ውርደት ላይ ጥለሃታልና ልትሸጣት ወይም እንደ ባሪያ ልትቈጥራት አይገባህም::

## የበኵር ልጅ መብት

[15]አንድ ሰው ሁለት ሚስቶች ቢኖሩት፤ አንደኛዋን የሚወዳት፣ ሌላዋን ግን የሚጠላት ቢሆን፣ ሁለቱም ወንዶች ልጆችን ወልደውለት በኵር ልጁ ግን የተወለደው ከማይወዳት ሚስቱ ቢሆን፣ [16]ንብረቱን ለልጆቹ በሚያወርስበት ጊዜ፣ የብኵርናን መብት ከማይወዳት ሚስቱ ከወለደው በኵር ልጅ ገፎ፣ ከሚወዳት ሚስቱ ለተወለደው ልጁ፣ በአድልዎ ማስጠት አይገባውም፤ [17]ይልቁንም ከተጠላችው ሚስቱ ለተወለደው ልጅ ካለው ሀብት ሁሉ ሁለት እጅ ድርሻውን በመስጠት ብኵርናውን ያስታ

10፥1፡11፥14
20፥18 ዘፀ10፥7፤ 34፥16
20፥20 ኤር6፥6
21፥1 ዘኍ25፥17
21፥3 ዘኍ19፥2
21፥5 ዘዳ48፥20፤ ዘፀ39፥43፡ዘዳ17፥8-11
21፥6 ማቴ27፥24
21፥8 ዘኍ35፥33-34
21፥9 ዘዳ19፥13
21፥10 ኢሱ21፥44፤ 1ነገ8፥46፡1ዜና9፥1፤ ዕዝ5፥12፡ኤር40፥1፤ ሕዝ1፥1፡17፥12፤ ዳን2፥25፡ሚክ4፥10
21፥11 ዘዳ6፥2፤ 34፥8
21፥12 ዘሌ14፥9፤ ዘኍ8፥7፡1ቆሮ11፥5
21፥13 መዝ45፥10
21፥14 ዘፍ34፥2
21፥15 ዘፍ4፥19፤ 29፥33
21፥16 1ዜና26፥10
21፥17 ዘፍ25፥31፤ 49፥3፡2ነገ2፥9፤ ኢሳ40፥2፡61፥7፤ ዘካ9፥12፡ሉቃ15፥12

[ጀ]17 የዕብራይጡ ቃል አንድን ነገር ወይም አንድን ሰው ሙሉ በሙሉ በማጥፋት ለእግዚአብሔር መስጠትን የሚያሳይ ነው::
[1]19 ወይም፣ *ለመከበብ ወረደ፤ የዛፎቹ ፍሬ ለሰው ጥቅም ይኖሉ*

20፥17 *ኬጢያዊውን ... ኢያቡሳዊውን፤* 7፥1 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 10፥6፡15-18፤ 13፥7 ማብ ይመ::

20፥19 *ዛፎቹን ... አታጥፋ፤* ከጊዜ በኋላ የተነሡ ጦረኞች ይህን መልካም ሕግ ባለመከተላቸው፣ አብዛኛው የፖለስቲና ምድር በረሓ ሊሆን ችሎአል (በአሁኑ ጊዜ በዚህ ምድር ዛፍ የማይገኘው በአብዛኛው ከቅርብ ጊዜ ወዲህ በተፈጠረ ሁኔታ ነው)::

21፥5 *እንዲያገለግሉ፤* እግዚአብሔር በሚመለክበት ስፍራ ሕዝቡን ወክለው በእግዚአብሔር ፊት እንዲቆሙ ማለት ነው (10፥8፤ 18፥5 ይመ):: *እንዲባርኩ፤* ዘኍ 6፥22-27 ይመ::

21፥6 *እጃቸውን ይታጠቡ፤* ከበደል ንጹሕ መሆንን የሚያመለክት ምሳሌያዊ አደራረግ ነው (ቍ 7፤ ማቴ 27፥24 ይመ)::

21፥10 *ከጠላቶችህ ጋር ጦርነት ልትገጥም፤* እዚህ ላይ የተጠቀሱት በከነዓን ምድር ዙሪያ የሚኖሩ ጠላቶች ናቸው (20፥14-15 ይመ)፤ በቍ 11 ላይ የተጠቀሰችውን ዐይነት ሴት ተማርካ ትወሰዳለች እንጂ ፈጽሞ አትጠፋም::

21፥12 *ጠጕርዋን ትላጭ፤* የቀድሞ ሕይወትዋን ትታ አዲስ ሕይወት መጀመሯን የሚያመለክት ወይም ደግሞ የሐዘን ምልክት (ቍ 13፤ ለምሳሌ ኤር 47፥5፤ ሚክ 1፥16 ይመ) ወይም የመዋረድ ምልክት (የኢሳ 7፥20 ማብ ይመ) ሊሆን ይችላል:: ለመንጻት ሥርዐትም ጠጕር መላጨት የተለመደ ነበር (ዘሌ 14፥8፤ ዘኍ 8፥7 ይመ፤ ከ2ሳሙ 19፥24 ጋር ያነጻጽሩ)::

21፥14 *ውርደት ላይ ጥለሃታልና፤* ይህን ሐሳብ ለመግለጽ በዚህ ስፍራ ከተጠቀሰው ሌላ ዐሥራ ሁለት ጊዜ ተብቶ የሚገኘው የዕብራይስጡ ቃል፣ ወንዶች ሴቶችን አስገድደው እንደሚደፍሩ የሚያመለክት ነው (22፥24፡29፤ ዘፍ 34፥2፤ መሳ 19፥24፤ 20፥5፤ 2ሳሙ 13፥12፡14፡ 22፡32፤ ሰቆ 5፥11፤ ሕዝ 22፥10-11)::

21፥15 *ሁለት ሚስቶች፤* የዘፍ 4፥19፤25፥6 ማብ ይመ::

21፥16 *በአድልዎ፤* ውርስ ይሰጥ የነበረው በልደት ቅደም ተከተል መሠረት እንጂ፣ በወላጆች አድልዎ አይደለም፤ ሆኖም ይህ ሕግ በመለኮት ፈቃድ አንዳንድ ጊዜ ተጥሶ ይገኛል (ለምሳሌ ያዕቆብ ወይም ሰሎሞን)::

21፥17 *ሁለት እጅ ድርሻውን፤* በእስራኤል አገር የበኵር ልጅ ከውርሱ ሁለት እጁን የመውሰድ መብት አለው:: ከእንዲህ ያለው ባሕል ጋር ተመሳሳይ የሆኑ ልማዶች በኑዚ፣ በጥንት ባቢሎናውያን ዘመን በነርሳ እንዲሁም በመካከለኛው የአሦራውያን ዘመን በአሦር ነበሩ:: በጥንት ሕዝቦች ዘንድ ይህ ዐይነቱ ልማድ የሕዝቡ መታወቂያ ነበር:: ከውርሱ ሁለት እጁን መውሰድ ማለት ደግሞ ሕጋዊ ተተኪ መሆን ማለት ነው:: ስለዚህም ኤልሳዕ

ውቅ፤ ያ ልጅ የአባቱ ኀይል መጀመሪያ ነውና፤ የብኵርና መብት የራሱ ነው::

### የማይታዘዝ ልጅ

[18]አንድ ሰው፣ የአባቱን ወይም የእናቱን ትእዛዝ የማይሰማ፣ ቢቀጡትም የማይታረም እልከኛና ዐመፀኛ ልጅ ቢኖረው፣ [19]አባትና እናቱ ይዘው በሚኖሩበት ከተማ በር ወዳሉት አለቆች ያምጡት፤ [20]"ይህ ልጃችን እልከኛና ዐመፀኛ ነው፤ አይታዘዘንም፤ አባካኝና ሰካራም ነው" ብለው ለአለቆች ይንገሯቸው:: [21]ከዚያም በኋላ የከተማዪቱ ሰዎች ሁሉ እስኪሞት ድረስ በድንጋይ ይውገሩት፤ ክፉውንም ከመ ካከልህ አስወግድ፤ እስራኤልም ሁሉ ይህን ሰምቶ ይፈራል::

### ልዩ ልዩ ሕጎች

[22]አንድ ሰው ለሞት የሚያበቃ በደል ፈጽሞ ቢገደልና በድኑ በዕንጨት ላይ ቢሰቀል፤ [23]በድኑን በዕንጨት ላይ እንደ ተሰቀለ አታሳ ድረው፤ ምክንያቱም በዕንጨት ላይ የተሰቀለ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ዘንድ የተረገመ ነውና፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ የሚሰጥህን ምድር እንዳታረክስ፣ በዚያኑ ዕለት ቅበረው::

**22** የወንድምህ በሬ ወይም በግ ጠፍቶ ሲባዝን ብታየው፣ ወደ እርሱ መልስህ አምጣለት እንጂ ዝም ብለህ አትለፈው፤ [2]ወን ድምህ በአቅራቢያህ ባይኖር፣ ወይም የማን መሆኑን የማታውቅ ከሆነ፣ ባለቤቱ ፈልጎት እስኪመጣ ድረስ፣ ወደ ቤትህ ወስደህ ከአ ንተ ዘንድ አቈየው፤ ከዚያም መልስህ ስጠው:: [3]የወንድምህን አህያ ወይም ልብስ ወይም የጠፋበትን ማናቸውንም ነገር ስታገኝ እንደዚሁ አድርግ፤ በቸልታ አትለፈው::

[4]የወንድምህ አህያ ወይም በሬ መንገድ ላይ ወድቆ ብታየው፣ በእግሩ እንዲቆምለት ርዳው እንጂ ዐልፈኸው አትሂድ::

[5]ሴት የወንድ ልብስ አትልበስ፤ ወንድም የሴት ልብስ አይልበስ፤ እንዲህ የሚያደርገውን ሁሉ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ይጸየፈ ዋልና::

[6]በመንገድ ስታልፍ፣ አንዲት ወፍ ጫጩቶቿን ወይም ዕንቁላሎቿን የታቀፈችበትን ጐጆ በዛፍ ወይም በመሬት ላይ ብታገኝ፣ እናቲቱን ከነጫ ጩቶቿ አትውሰድ፤ [7]ጫጩቶቿን መውሰድ ትች ላለህ፤ እናቲቱን ግን መልካም እንዲሆንልህና ዕድሜህም እንዲረዝም ልቀቃት፤

[8]አዲስ ቤት በምትሠራበት ጊዜ፣ ከጣራው ላይ ሰው ወድቆ በቤትህ ላይ የደም በደል እንዳታመጣ፣ በጣራው ዙሪያ መከታ አብጅለት::

[9]በወይን ተክል ቦታህ ውስጥ ሁለት ዐይነት ዘር አትዝራ፤ ይህን ካደረግህ፣ የዘራኸው ሰብል ብቻ ሳይሆን፣ የወይን ፍሬህም ይጠፋል::

[10]በሬና አህያ በአንድ ላይ ጠምደህ አትረስ::

[11]ሱፍና በፍታ አንድ ላይ ተፈትሎ የተሠራ ልብስ አትልበስ::

[12]በምትለብሰው ልብስ ላይ በአራቱ ማእዘኖች ዘርፍ አድርግ::

### ጋብቻን በንጽሕና ስለ መጠበቅ

[13]አንድ ወንድ ሚስት አግብቶ አብሮአት ከተኛ በኋላ ቢጠላት፣ [14]ስሟንም በማጥፋት፣ "ይህችን ሴት አገባኋት፤ ዳሩ ግን በደረስሁባት ጊዜ ድንግልናዋን አላገኘሁም" ቢል፣ [15]የልጂቱ አባትና እናት ድንግልናዋን የሚያረጋግጥ ማስረጃ ይዘው በከተማዪቱ በር ወዳሉት አለቆች ይምጡ:: [16]የልጂቱም አባት ለአለቆቹ እንዲህ ይበል፤ "ልጄን ለዚህ ሰው ዳርሁለት፤ እርሱ ግን ጠላት፤ [17]ስሟንም በማጥፋት፣ 'ልጅህን ከነድንግልናዋ አላገኘኋትም' ብሎኛል፤ ነገር ግን የልጄ ድንግልና ማረጋገጫ ይኸውላችሁ!" ከዚያም ወላጆቿ የደሙን ሸማ በከተማዪቱ አለቆች ፊት ይዘርጉት:: [18]ከዚያም በኋላ አለቆቹ ሰውየውን ይዘው ይቅጡት፤ [19]ይህ ሰው የአንዲት እስራኤላዊት ድንግል ስም አጥፍቶአልና አንድ መቶ ሰቅል[a] ብር ያስከፍሉት፤ ገንዘቡንም ለልጂቱ አባት ይስጡት፤ ሴቲቱም ሚስቱ

[a]19 ወደ አንድ ኪሎ ግራም ነው::

21፥18 ዘፍ31፥35፤ ምሳ1፥8፤30፥17፤ መዝ78፥8፤ ኢሳ30፥1፤ ኤር5፥23፤ሶፎ3፥1፤ ኤፌ6፥1-3
21፥21 ዘሌ20፥9፤ ዘዳ13፥11፤19፥19፤1 ቆሮ5፥13
21፥22 ዘዳ22፥26፤ ማቴ26፥66፤ ማር14፥64፤ ሐሥ23፥29
21፥23 ዘሌ18፥25፤ ኢያ8፥29፤10፥27፤ ዕዝ6፥11፤አስ2፥23፤ 7፥9፤8፥7፤9፥13፡25፤ ኢሳ50፥11፤ ሕዝ39፥12፤ ዮሐ19፥31፤ገላ3፥13፤
22፥1 ዘፀ23፥4-5፤ ምሳ27፥10፤ዘካ7፥9
22፥4 ዘፀ23፥5፤ 1ቆሮ9፥9
22፥6 ዘሌ22፥28፤
22፥7 ዘሌ22፥28፤ ዘዳ5፥29
22፥8 ኢያ2፥8፤ 1ሳሙ9፥25፤ 2ሳሙ11፥2
22፥9 ዘሌ19፥19
22፥10 2ቆሮ6፥14
22፥11 ዘሌ19፥19
22፥12 ዘኍ15፥37-41፤ ማቴ23፥5
2፥13 ዘዳ24፥1
22፥15 ዘፍ23፥10
22፥18 ዘፀ18፥21፤ ዘዳ1፥9-18

በኤልያስ ቦታ ተተካ (2ነገ 2፥9):: *የአባቱ ኀይል መጀመሪያ ነውና፤* የአንድ ሰው ዘር የመተካት ችሎታው የመጀመሪያ ውጤት ነው::

21፥18 *የአባቱን ወይም የእናቱን ትእዛዝ የማይሰማ ... እልከኛና ዐመፀኛ፤* ከዐሥርቱ ትእዛዛት መካከል አምስተኛውን ትእዛዝ በግልጽ የሚጻረር እኩይ ተግባር ነው (5፥16፤ ዘፀ 20፥12 እና ማብ ይመ)::

21፥21 *በድንጋይ ይውገሩት፤* 5፥16፤ 27፥16፤ ዘፀ 21፥15፡17 ይመ:: *ክፉውንም ከመካከልህ አስወግድ፤* የ13፥5 ማብ ይመ::

21፥22 *ቢገደልና በድኑ በዕንጨት ላይ ቢሰቀል፤* በደል ፈጽሞ የተገኘው ሰው በመጀመሪያ ከተገደለ በኋላ፣ 'ዕንጨት ላይ ይሰቀላል' (ዘፍ 40፥19 ይመ)፤ ወይም ይህን ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ በግልጽ እንደሚያስረዳው፣ "በሹል ምሰሶ ላይ ይሰካል" (የዘፍ 40፥19፤ የአስ 2፥23 ማብ ይመ)::

21፥23 *በድኑን በዕንጨት ላይ እንደተሰቀለ አታሳድረው፤* በድኑን ለረጅም ጊዜ እንዲታይ ማድረግ ለወንጀሉም ሆነ ለወንጀለ ኛው ከሚገባው በላይ ትኵረት እንዲሰጥ ያደርጋል:: *በእግዚአብሔር ዘንድ የተረገመ፤* እግዚአብሔር ነፍስ መግደልን በፍጹም ይቃወማል፤ በዕንጨት ላይ መሰቀል የእግዚአብሔርን ፍርድና በእርሱም መተውን ያመለክታል:: ክርስቶስ የኀጢአታችንን ሙሉ ቅጣት ተቀበለ፤ ስለዚ ህም በእኛ ምትክ "ርግማን ሆነ" (ገላ 3፥13)::

22፥1 *ዝም ብለህ አትለፈው፤* ቍ 3-4 ይመ:: በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የምናገኛቸው ሕጎች የተሰጡት፣ እኩይ ባሕርይንና ተግባርን ለመቅጣት ብቻ ሳይሆን፣ አንድ ሰው ለሌላው ሰውና ንብረት ጥንቃቄ እንዲያደርግ ጭምር ነው:: በገጽ 273 ላይ "በኪዳኑ ውስጥ ለሚገኙ ዋና ዋና ማኅበራዊ ጕዳዮች የሚደረግ ጥንቃቄ" በሚል የተጻፈው ሠንጠረዥ ይመ::

*22፥5፤* ይህ ሕግ የወጣው፣ ምናልባት በሃይማኖት ስምና ሽፋን የተቃራኒን ጾታ ልብስ በመልበስ የግብረ ሥጋ ፍላጎት ለማር ካት የሚደረገውን ስውር ስሜት ወይም የግብረ ሰዶምን ተግባር ለመከላከል ነው:: እግዚአብሔር በወንድና በሴት መካከል እንዲ ኖር ያደረገውን ልዩነት እንደሌለ መቍጠር ተገቢ አይደለም (ዘሌ 18፥22፤ 20፥13 ይመ)::

22፥14 *ድንግልናዋን አላገኘሁም፤* ለድንግልናዋ ማስረጃ የሚሆን ደም የነካው ልብስ ወይም ጨርቅ ማለት ነው (ቍ 15፡17፡20 ይመ)::

22፥15 *በከተማዪቱ በር ወዳሉት አለቆች፤* 25፥7 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 19፥1፤ የሩት 4፥1 ማብ ይመ::

22፥19 *አንድ መቶ ሰቅል ብር፤* ይህን ያህል ቅጣት መክፈል ከባድ ነው፤ ሆሴዕ ሚስቱን ጎሜርን ለ 'መግዛት' ካወጣው (ሆሴ 3፥2) ወይም ኤርምያስ በዓናቶት ያለውን እርሻ ለመግዛት ካወጣው ገንዘብ በብዙ ዕጥፍ ይበልጣል (ኤር 32፥9):: ይህም ለአንዲት ልጃገረድ ማጫ ከሚከፈለው አማካይ ገንዘብ በሁለት ዕጥፍ ከፍ ያለ ነው (የቍ 29 ማብ ይመ):: ይህ ከፍተኛ ቅጣትና ፍቺን የሚከለክለው ሕግ

ሆና ትኖራለች፤ በሕይወት ዘመኑ ሁሉ ሊፈታት አይችልም::

[20]ሆኖም ክሱ እውነት ሆኖ ሴቲቱ ድንግል ለመሆኗ ምንም ማረጋገጫ ማቅረብ ካልተቻለ፣ [21]ገና በአባቷ ቤት ሳለች በማመንዘር በእስራ ኤል ውስጥ ወራዳ ተግባር ፈጽማለችና ወደ አባቷ ቤት ደጃፍ ያምጧት፤ እዚያም የከተ ማዋ ሰዎች እስክትሞት ድረስ በድንጋይ ይውገሯት:: ክፉውን ከመካከልህ ማስወገድ አለብህ::

[22]አንድ ሰው፣ ከሌላ ሰው ሚስት ጋር ተኝቶ ቢገኝ፣ አብሮአት የተኛው ሰውና ሴቲቱ ሁለ ቱም ይገደሉ፤ ክፉውን ከእስራኤል ማስወገድ አለብህ::

[23]አንድ ሰው የታጨች ድንግል በከተማ ውስጥ አግኝቶ ከእርሷ ጋር ቢተኛ፣ [24]ልጃ ገረዲቱ በከተማ ውስጥ እያለች አስጥሉኝ ብላ ስላልጮኸች፣ ሰውየውም የሌላን ሰው ሚስት አስገድዶ ስለ ደፈረ፣ ሁለቱንም ወደ ከተማ ደጃፍ ወስዳችሁ እስኪሞቱ ድረስ በድንጋይ ውገሯቸው:: ክፉውን ከመካከልህ ማስወገድ አለብህ::

[25]ነገር ግን አንድ ሰው የታጨችውን ልጃ ገረድ ከከተማ ውጭ አግኝቶ በማስገደድ ቢደ ፍራት፣ ይህን ድርጊት የፈጸመው ሰው፣ ብቻ ይገደል:: [26]በልጃገረዲቱ ላይ ግን ምንም አታድርጉባት፤ ለሞት የሚያበቃ ኃጢአት ምንም አልሠራችም፤ ይህ ዐይነቱ ጉዳይ፣ አደጋ ጥሎ ባልንጀራውን ከሚገድል ሰው አድራ ጎት ጋር የሚመሳሰል ነው:: [27]ምክንያቱም ሰውየው የታጨችውን ልጃገረድ ከከተማ ውጭ ስላገኛትና ብትጮኽም እንኳ ለርዳታ የደረሰላት ማንም ሰው ስላልነበር ነው::

[28]አንድ ሰው ያልታጨች ልጃገረድ አግኝቶ በማስገደድ ቢደርስባትና ቢጋለጡ፣ [29]ሰውየው ለልጅቷ አባት አምሳ ሰቅል[a] ብር ይክፈል፤ ልጃገረዲቱን አስገድዶ ደፍሮአታልና እርሷን

22፥20 ዘዳ17፥4
22፥21 ዘፍ34፥7፤ 38፥24፤ዘሌ19፥29፤ ዘዳ23፥17-18፤ 1ቆሮ5፥13
22፥22 ዘፍ38፥24፤ ዘፀ21፥12፤ 2ሳሙ11፥4፤ ማቴ5፥27-28፤ ዮሐ8፥5፤1ቆሮ6፥9፤ ዕብ13፥4
22፥24 1ቆሮ5፥13
22፥27 ዘፍ39፥14
22፥28 ዘፀ20፥7፤ 34፥16

[a]29 ወደ 0.6 ኪሎ ግራም ነው::

የወጣው፣ ባል ሚስቱን በሆነ ባልሆነው እንዳይከስና ድንገት ብድግ ብሎ እንዳይፈታ ለመከላከል ነው::

22፥21፡24 *ክፉውን ከመካከልህ ማስወገድ አለብህ* ቍ 22 ይመ፤ እንዲሁም የ13፥5 ማብ ይመ::

*22፥22* ዘሌ 20፥10 ይመ::

22፥29 *አምሳ ሰቅል ብር*፤ ምናልባት በአማካይ ለአንዲት ልጃገረድ የሚከፈለውን ማጫ ያህል ይሆናል፤ ሆኖም እንደየሰው ዐቅም ሊለያይ ይችላል (የዘፀ 22፥16 ማብ ይመ)::

22፥30 *የአባቱን ሚስት*፤ ከእናቱ ሌላ አባቱ ያገባትን ሴት ለማለት ነው (27፥20 ይመ):: *የአባቱን መኝታ አያርክስ*፤ ቃል በቃል

## በኪዳኑ ውስጥ ለሚገኙ ዋና ዋና ማኅበራዊ ጉዳዮች የሚደረግ ጥንቃቄ

1. **ሰብእና**
   የእያንዳንዱ ሰው ሰብእና መጠበቅ አለበት (ዘፀ 20፥13፤ 21፥16-21፡26-31፤ ዘሌ 19፥14፤ ዘዳ 5፥17፤ 24፥7፤ 27፥18)::

2. **የሐሰት ውንጀላ**
   እያንዳንዱ ሰው ከስድብና ከሐሰት ውንጀላ የተጠበቀ ነው (ዘፀ 20፥16፤ 23፥1-3፤ ዘሌ 19፥16፤ ዘዳ 5፥20፤ 19፥15-21)::

3. **ሴቶች**
   ሴት በኅብረተሰቡ ውስጥ በጥገኝነት ስፍራ ብትገኝም ምንም ዓይነት በደል ሊደርስባት አይገባም (ዘፀ 21፥7-11፡ 20፡26-32፤ 22፥16-17፤ ዘዳ 21፥10-14፤ 22፥13-30፤ 24፥1 -5):: ከጥፋቱ መጠን በላይ መቀጣት

4. **ቅጣት**
   ጥፋተኛው (ዘዳ 25፥1-5) የለበትም::

5. **ክብር**
   የእያንዳንዱን እስራኤላዊ የእግዚአብሔር ነጻ ሰውና አገልጋይ የመሆን ክብርና መብት አለው፤ ይህ መብት ይጠ በቃል (ዘፀ 21፥2፡5-6፤ ዘሌ 25፤ ዘዳ 15፥12-18)::

6. **ውርስ**
   የእያንዳንዱ እስራኤላዊ በተስፋዪቱ ምድር ያለው ውርስ የተጠበቀ ነው (ዘሌ 25፤ ዘኍ 27፥5-7፤ 36፥1-9፤ ዘዳ 25፥5 -10)::

7. **ንብረት**
   የእያንዳንዱ እስራኤላዊ ንብረት የተጠበቀ ነው (ዘፀ 20፥15፤ 21፥33-36፤ 22፥1-5፤ 23፥4-5፤ ዘሌ 19፥35-36፤ ዘዳ 5፥19፤ 22፥1-4፤ 25፥13-15)::

8. **የሥራ ፍሬ/ዋጋ**
   እያንዳንዱ የሥራውን ፍሬ የማግኘት መብት አለው (ዘሌ 19፥13፤ ዘዳ 24፥14፤ 25፥4፤ )::

9. **የምድር ፍሬ**
   እያንዳንዱ ሰው ምድር ያበቀለችውን/ያፈራችውን ፍሬ መካፈል ይችላል (ዘፀ 23፥10-11፤ ዘሌ 19፥9-10፤ 23፥22፣ 25፥3-55፤ ዘዳ 14፥28-29፤ 24፥19-21)::

10. **የሰንበት ዕረፍት**
    እያንዳንዱ ሰው እስከ ዝቅተኛው አገልጋይ ድረስ ያለው ሳምንታዊውን የእግዚአብሔርን ሰንበት መካፈል/ማረፍ ይገባዋል (ዘፀ 23፥12፤ 28፥8-11፤ ዘዳ 5፥12-15)::

11. **ጋብቻ**
    ጋብቻ በቅድስና መጠበቅ ይኖርበታል (ዘፀ 20፥14፤ ዘሌ 18፥6-23፤ 20፥10-21፤ ዘዳ 5፥18፤ 22፥13-30)::

12. **ብዝበዛ**
    ማንም ሰው ዐቅም የሌለው፣ ድኻ ወይም ደካማ ቢሆን እንኳ መጨቈን ወይም መበዝበዝ የለበትም (ዘፀ 22፥21-27፤ ዘሌ 19፥14፡ 33-34፤ 25፥35-36፤ ዘዳ 23፥19፤ 24፥6፡12-15፡17፤ 27፥18)::

13. **ቅን ፍርድ**
    ማንኛውም ሰው ወደ ፍርድ ችሎት የመቅረብና አቤቱታ የማቅረብ እንዲሁም ቅን ፍርድ የማግኘት መብት አለው (ዘፀ 23፥6፡8፤ ዘሌ 19፥15፤ ዘዳ 1፥17፤ 10፥17-18፤ 16፥18 -20፤ 17፥8-13፤ 19፥15-21)::

13. **ቅን ፍርድ**
    ማንኛውም ሰው ወደ ፍርድ ችሎት የመቅረብና አቤቱታ የማቅረብ እንዲሁም ቅን ፍርድ የማግኘት መብት አለው (ዘፀ 23፥6፡8፤ ዘሌ 19፥15፤ ዘዳ 1፥17፤ 10፥17-18፤ 16፥18-20፤ 17፥8-13፤ 19፥15-21)::

14. **ማኅበራዊ ሥርዓት**
    እያንዳንዱ ሰው በኅብረተሰቡ ውስጥ እግዚአብሔር የሰጠው ስፍራ መከበር አለበት (ዘፀ 20፥12፤ 21፥15፡17፤ 22፥28፤ዘሌ 19፥3፡32፤ 20፥9፤ ዘዳ 5፥16፤17፥8-13፤ 21፥15-21፤ 27፥16)::

15. **ሕግ**
    ማንኛውም ሰው፣ ንጉሥ እንኳ ቢሆን ከሕግ በላይ ሊሆን አይችልም (ዘዳ 17፥18-20)::

16. **እንስሳት**
    ለእንስሳት ጥበቃና እንክብካቤ ማድረግ ከሁሉ ሰው ይጠበቃል (ዘፀ 23፥5፡11፤ ዘሌ 25፥7፤ ዘዳ 22፥4፡6-7፤ 25፥4)::

ማግባት አለበት፤ በሕይወት ዘመኑ ሁሉ ሊፈ ታት አይችልም።

30 አንድ ሰው የአባቱን ሚስት ማግባት የለበትም፤ የአባቱንም መኝታ አያርክስ።

## ከእግዚአብሔር ጉባኤ መለየት

**23** ብልቱ የተቀጠቀጠ ወይም የተቈረጠ ማናቸውም ሰው ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጉባኤ አይግባ።

2 ዲቃላም ይሁን የዲቃላው ዘር የሆነ ሁሉ፣ እስከ ዐሥር ትውልድ ድረስ እንኳን ቢሆን ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጉባኤ አይግባ።

3 አሞናዊም ሆነ ሞዓባዊ ወይም ማናቸውም የእርሱ ዘር፣ እስከ ዐሥር ትውልድ እንኳ ቢሆን ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጉባኤ አይግባ። 4 ምክንያቱም ከግብፅ ከወጣችሁ በኋላ በጕዞ ላይ በነበራችሁበት ጊዜ እህል ውሃ ይዘው አልተቀበሏችሁም፤ በመስጴጦምያ በምትገኘው በፐቶር* ይኖር የነበረውን የቢዖርን ልጅ በለዓምም አንተን እንዲረግም በገንዘብ ገዙት። 5 ይሁን እንጂ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በለዓምን አልሰማውም፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ስለሚወድህ ርግማኑን በረከት አደረገልህ። 6 በሕይወት ዘመንህ ሁሉ ሰላምን ለእነርሱ አትመኝ።

7 ወንድምህ ስለ ሆነ ኤዶማዊውን አትጸየፈው፤ መጻተኛ ሆነህ በአገሩ ኖረሃልና ግብፃዊውን አትጥላው። 8 ለእነርሱ የተወለዱላቸው የሦስተኛው ትውልድ ልጆች ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ጉባኤ መግባት ይችላሉ።

## የጦር ሰፈር ንጽሕና አጠባበቅ

9 ጠላትህን ለመውጋት ወጥተህ በሰፈርህ ጊዜ፤ ከማናቸውም ርኵሰት ራስህን ጠብቅ። 10 ከመካከላችሁ ሌሊት ዘር በማፍሰስ የረከሰ ሰው ቢኖር ከሰፈር ወጥቶ እዚያው ይቈይ። 11 እየመሸ ሲመጣ ግን ገላውን ይታጠብ፤ ፀሐይ ስትጠልቅም ወደ ሰፈሩ ይመለስ።

12 ለመጸዳጃ የሚሆንህን ቦታ ከሰፈር ውጭ አዘጋጅ። 13 ከትጥቅህም ጋር መቈፈሪያ ያዝ፤ በምትጸዳዳበት ጊዜ ዐፈር ቈፍረህ በዐይነ ምድርህ ላይ መልስበት። 14 *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ሊጠብቅህ ጠላቶችህንም በእጅህ አሳልፎ ሊሰጥህ በሰፈር ውስጥ ስለሚዘዋወር፣ በመካከልህ አንዳች ነውር አይቶ ከአንተ እንዳይመለስ፣ ሰፈርህ የተቀደሰ ይሁን።

## ልዩ ልዩ ሕጎች

15 አንድ ባሪያ ከአሳዳሪው ኰብልሎ ወደ አንተ ቢመጣ፣ ለአሳዳሪው አሳልፈህ አትስጠው። 16 ደስ በሚያሰኘው ቦታና ራሱ በመረጠው ከተማ በመካከልህ ይኑር፤ አንተም አታስጨንቀው።

17 ወንድ ወይም ሴት እስራኤላዊ የቤተ ጣዖት አመንዝራ አይሁን። 18 ለዝሙት አዳሪ ሴት ወይም ለወንደቃ* የተከፈለውን ዋጋ ለማናቸውም ስእለት አድርገህ ለመስጠት ወደ *አምላክህ* ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ቤት አታምጣ፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ሁለቱንም ይጸየፋቸዋልና።

19 የገንዘብ፣ የእህል ወይም የማንኛውንም ነገር ወለድ ለማግኘት ለወንድምህ በወለድ አታበድር። 20 ባዕድ ለሆነ ሰው ወለድ ማበደር ትችላለህ፤ ነገር ግን ልትወርሳት በምትገባባት ምድር እጅህ በሚነካው በማናቸውም ነገር *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንዲባርክህ ለእስራኤላዊ ወንድምህ በወለድ አታበድረው።

21 *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ስእለት ከተሳልህ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) አጥብቆ ከአንተ ይሻዋልና፣ ኀጢአት እንዳይሆንብህ ለመክፈል አትዘግይ። 22 ሳትሳል ብትቀር ግን በደለኛ አትሆንም። 23 በአንደበትህ የተናገርኸውን ሁሉ ለመፈጸም ጠንቃቃ ሁን፤ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በገዛ አንደበትህ ፈቅደህ ስእለት ተስለሃልና።

24 ወደ ባልንጀራህ የወይን ተክል ቦታ በምትገባበት ጊዜ፣ ያሰኘህን ያህል መብላት ትችላለህ፤ ነገር ግን አንዳችም በዕቃህ አትያዝ። 25 ወደ ባልንጀራህ ዕርሻ በምትገባበት ጊዜ፣ እሸት መቅጠፍ ትችላለህ፤ በሰብሉ ላይ ግን ማጭድ አታሳርፍበት።

22፥30 ዘፍ29፥29፤ ዘሌ.18፥8፤20፥9፤ 1ቆሮ5፥1
23፥1 ዘሌ.21፥20
23፥3 ቊ4፤ ዘፍ19፥38፤ነህ13፥2
23፥4 ቊ3፤ ዘፍ24፥10፤ዘኍ23፥7፤ ዘዳ2፥28፤2ጴጥ2፥15
23፥5 ዘኍ24፥10፤ ዘዳ4፥37፤ ኢሱ24፥10፤ ምሳ26፥2
23፥6 ዘኍ24፥17፤ ዕዝ9፥12፤ ኢሳ15፥1፤25፥10፤ ኤር25፥21፤27፥3፤ 48፥1፤ሕዝ25፥8፤ ሶፎ2፥9፤ማቴ5፥43
23፥7 ዘፍ25፥26፡ 30፤ዘሌ.19፥34
23፥9 ዘሌ.15፥1-33
23፥10 ዘሌ.15፥16
23፥11 ዘሌ.15፥16፤ 1ሳሙ21፥5
23፥14 ዘፍ3፥8፤ ዘፀ3፥5
23፥15 2ሳሙ22፥3፤ 1ሳሙ30፥15፤ መዝ2፥12፤71፥1
23፥16 ዘፀ22፥21፤ 23፥6
23፥17 ዘፍ38፥21፤ 1ነገ14፥24፤15፥12፤ 22፥46፤2ነገ23፥7፤ ኢዮ36፥14
23፥18 ዘፍ19፥5፤ ዘሌ.20፥13፤ ራእ22፥15
23፥19 ዘሌ.25፥35-37፤ነህ5፥2-7
23፥20 ዘፍ31፥15፤ ዘዳ15፥3፡10
23፥21 ዘኍ6፥21፤ 30፥1-2፤መሳ11፥35፤ ኢዮ22፥27፤ መዝ15፥4፤61፥8፤ 65፥1፤76፥11፤ መክ5፥4-5፤ ኢሳ19፥21፤ማቴ5፥33፤ ሐሥ5፥3፤
23፥22 ሐሥ5፥4
23፥25 ማቴ 12፥1፤ ማር2፥23፤ሉቃ6፥1

*4 ይኸውም ሰሜን ምዕራብ መስጴጦምያ ነው።
*18 ዕብራይስጡ፣ ውሻ ይላል።

ከተወሰደ፣ 'የአባቱን ልብስ ጫፍ አይግለጥ' ማለት ነው (የሩት 3፥9፤ የሕዝ 16፥8 ማብ ይመ)።

*23፥11* ጃንደረባ ለሆኑ ሰዎች ከጊዜ በኋላ የተሰጠውን በረከት በኢሳ 56፥4-5፤ ሐሥ 8፥26-39 ላይ ይመ።

23፥2-3 *እስከ ዐሥር ትውልድ ድረስ፤* 'ዐሥር' ቍጥር ሙሉነትን ወይም ፍጻሜን የሚያመለክት ቃል በመሆኑ እስከ ዘላለም ማለት ሊሆን ይችላል። ከዚህ ሐረግ ጋር አቻ አገላለጽ ያለው ሐረግ በቍ 6 ላይ "በሕይወት ዘመንህ ሁሉ" ተብሎ ተጠቅሷል (ቃል በቃል ሲተረጐም "ዕድሜህን ሙሉ ለዘላለም" ማለት ነው)።

*23፥3፤* ሞዓባውያን ወደ እግዚአብሔር ሕዝብ ጉባኤ እንዳይገቡ የተከለከሉ ቢሆንም፣ ሩት ግን ልዩ ዕድል አግኝታለች (በሩት መጽሐፍ መግቢያ ላይ "መሪ ሐሳብና ሥነ መለኮታዊ ይዘት"የሚለውን ይመ)።

23፥4 *የቢዖር ልጅ በለዓም፤* ዘኍ 22፥4-24፥25 ይመ።

23፥6 *ሰላምን ለእነርሱ አትመኝ፤* ነቢያት በሞዓብ፣ በአሞንና በኤዶም ላይ የተናገሩትን የፍርድ ቃል ይመ (ኢሳ 15፥16፤ ኤር 48፥1-49፥6፤ ሕዝ 25፥1-11፤ አሞ 1፥13-2፥3፤ ሶፎ 2፥8-11 ይመ)።

23፥7 *ወንድምህ ስለ ሆነ ኤዶማዊውን፤* ኤዶም (ዔሳው) ከወንድሙ ከያዕቆብ (ከእስራኤል) ጋር በነበረው ጠብ ምክንያት ብዙ ጊዜ ተዘግቦአል፤ (አሞ 1፥11፤ አብ 10 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 25፥22፡26 ማብ ይመ)።

*23፥9-14፤* የእስራኤልን ጦር ሰፈር በንጽሕና ስለ መጠበቅ የተሰጠ መመሪያ ነው። በአጠቃላይ ሕዝቡን በተመለከተ የተሰጠውን ተመሳሳይ መመሪያ በዘሌ 15 ላይ ይመ።

23፥15 *አንድ ባሪያ ከአሳዳሪው ኰብልሎ ወደ አንተ ቢመጣ፤* አንድ ከሌላ አገር የመጣ ባሪያ በእስራኤል አገር ነጻ ሆኖ ለመኖር ከፈለገ ማለት ነው (ቍ 16 ይመ)፤ ከ24፥7 ጋር ያነጻጽሩ።

*23፥17-18፤* የዘፀ 34፥15፤ መሳ 2፥17 ማብ ይመ። ማብ ይመ።

23፥18 *ወንደቃ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ውሻ" ማለት ሲሆን፣ ቃሉ አብዛኛውን ጊዜ ንጽሕና ከጐደለው ምግባር ወይም መንፈሳዊነት ጋር የተያያዘ ነው (ከ7፥6፤ 15፥26፤ ከፊል 3፥2 ጋር ያነጻጽሩ)።

23፥19 *ወለድ፤* የዘፀ 22፥25-27፤ የዘሌ 25፥36 ማብ ይመ።

23፥20 *ባዕድ ለሆነ ሰው በወለድ ማበደር ትችላለህ፤* አንድ የውጭ አገር ነጋዴ ወደ እስራኤል የሚመጣው ለራሱ ጥቅም ብሎ ስለሆነ ወለድ መክፈል አለበት።

*23፥21-23፤* የዘኍ 30 ማብ ይመ፤ እንዲሁም መክ 5፥4-6 ይመ።

**24** አንድ ሰው አንዲት ሴት ካገባ በኋላ፣ አሳፋሪ ነገር አግኝቶባት ባይደሰት ባት፣ የፍቺ ወረቀት ጽፎ በመስጠት ከቤቱ አስወጥቶ ይስደዳት። [2]ከቤቱ ከወጣች በኋላ ሌላ ባል ብታገባ፣ [3]ሁለተኛ ባሏም እንደዚሁ ጠልቷት የፍቺ ወረቀት በመስጠት ከቤቱ አስወጥቶ ቢሰዳት ወይም ቢሞት፣ [4]ከዚያ በኋላ የፈታት የመጀመሪያ ባሏ፣ የረከሰች በመሆኗ እንደ ገና መልሶ ሊያገባት አይችልም፤ ይህ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት አስጸያፊ ነው። *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድር ላይ ኀጢአት አታምጣ።

[5]አዲስ ሚስት በቅርብ ጊዜ ያገባ ሰው፣ ለጦርነት አይሂድ፤ ወይም ሌላ ሥራ እንዲሠራ አይገደድ። ለአንድ ዓመት ነጻ ሆኖ እቤቱ ይቈይ፤ ያገባትን ሚስቱን ደስ ያሰኛት።

[6]ወፍጮና መጁን ወይም መጁንም እንኳ ቢሆን፣ የብድር መያዣ አድርገህ አትውሰድ፤ የሰውን ነፍስ መያዣ አድርጎ መውሰድ ይሆናልና።

[7]አንድ ሰው ከእስራኤላውያን ወንድሞቹ አንዱን ፈንግሎ በመውሰድ ባሪያ ሲያደርገው ወይም ሲሸጠው ቢገኝ፣ ፈንጋዩ ይሙት። ክፉውን ከመካከልህ አስወግድ።

[8]የለምጽ ደዌን* በተመለከተ ሌዋውያን ካህናት የሚሰጡህን መመሪያ በትክክል ለመፈጸም ጥንቃቄ አድርግ። እኔ ለእነርሱ የሰጠሁትን ትእዛዝ በጥንቃቄ ተከተል። [9]ከግብፅ ከወጣችሁ ኋላ በመንገድ ላይ ሳላችሁ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በማርያም ላይ ያደረገባትን አስታውሱ።

[10]ማናቸውንም ነገር ለባልንጀራህ ስታበድር መያዣ አድርጎ የሚሰጥህን ለመቀበል ወደ ቤቱ አትግባ። [11]አንተ ከውጭ ሆነህ ጠብቅ፤ ያበደርኸውም ሰው መያዣውን ከቤት ያምጣልህ። [12]ሰውየው ድኻ ከሆነ፣ መያዣውን ከአንተ ዘንድ አታሳድርበት። [13]መደረቢያውን ለብሶት እንዲያድር ፀሓይ ሳትጠልቅ መልስለት። ከዚያም ያመሰግንሃል፤ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊትም የጽድቅ ሥራ ሆኖ ይቈጠርልሃል።

[14]ድኻና ችግረኛ የሆነውን የምንዳ ሠራተኛ እስራኤላዊ ወንድምህም ሆነ፣ ከከተሞችህ ባንዲቱ የሚኖረውን መጻተኛ አትበዝብዘው፤ [15]የሠራበትን ሒሳብ በዕለቱ፣ ፀሓይ ሳትጠልቅ ክፈለው፤ ድኻ በመሆኑ በጕጕት ይጠባበቀዋልና። ያለበለዚያ ወደ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ይጮኽና ኀጢአት ይሆንብሃል።

[16]አባቶች ስለ ልጆቻቸው፣ ልጆችም ስለ አባቶቻቸው አይገደሉ፤ እያንዳንዱ በራሱ ኀጢአት ይገደል።

[17]ለመጻተኛው ወይም አባት ለሌለው ልጅ ፍትሕ አትንፈገው፤ የመበለቲቱንም መደረቢያ መያዣ አታድርግ። [18]አንተም በግብፅ ባሪያ እንደ ነበርህና *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከዚያ እንደ ተቤዠህ አስታውስ፤ ይህን እንድታደርግ ያዘዝሁህ ለዚህ ነው።

[19]የዕርሻህን ሰብል በምታጭድበት ጊዜ፣ ተረስቶ የቀረ ነዶ ቢኖር፣ ያን ለመውሰድ ተመልሰህ አትሂድ። *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጅህ ሥራ ሁሉ እንዲባርክህ ነዶውን ለመጻተኛው፣ አባት ለሌለውና ለመበለቲቱ ተወው። [20]የወይራ ዛፍህን ፍሬ በምታራግፍበት ጊዜ በየቅርንጫፉ ላይ የቀረውን ለመቃረም ተመልሰህ አትሂድ፤ ለመጻተኛው፣ አባት ለሌለውና ለመበለቲቱ ተወው። [21]የወይን ተክልህን ፍሬ ስትሰበስብ ቃርሚያውን ለመሰብሰብ አትመለስበት፤ የቀረውን ለመጻተኛው፣ አባት ለሌለውና ለመበለቲቱ ተወው። [22]በግብፅ ባሪያ እንደ ነበርህ አስታውስ፤ ይህን እንድታደርግ ያዘዝሁህ ለዚህ ነው።

**25** በሰዎች መካከል ጠብ ቢነሣና ወደ ፍርድ አደባባይ ቢሄዱ፣ ዳኞች ተበዳይን ነጻ፣ በዳይን ግን ጥፋተኛ በማድረግ የፍርድ ውሳኔ ይስጡ። [2]በደለኛው ሰው መገረፍ የሚገባው ሆኖ ከተገኘ፣ ዳኛው መሬት ላይ ያጋድመው፤ ለጥፋቱ ተመጣጣኝ የሆነ ግርፋት እርሱ ባለበት ይገረፍ። [3]ሆኖም ግርፋቱ ከአርባ የሚበልጥ አይሁን፤ ከዚህ ካለፈ ግን፣ ወንድምህ በፊትህ የተዋረደ ይሆናል።

[4]እህል እያበራየ ያለውን በሬ አፉን አትሰር።

[5]ወንድማማቾች በአንድነት ቢኖሩና ከእነርሱ አንዱ ወንድ ልጅ ሳይወልድ ቢሞት፣ የሚቹ ሚስት ከቤተ ሰቡ ውጭ ባል ማግባት የለባትም። የባሏ ወንድም ይውሰዳትና ያግባት፤ የዋርሳነት ግዴታውንም ይፈጽምላት። [6]በመጀመሪያ

*8 ዕብራይስጡ ለምጽን ብቻ ሳይሆን ቆዳን የሚያጠቁትን ማናቸውንም ዐይነት በሽታዎች ያመለክታል።

24፥1 ቍ3፤ ዘዳ22፥13፤2ነገ17፥6፤ ኢሳ50፥1፤ኤር3፥8፤ ሚል2፥16፤ ማቴ1፥19፤5፥31፤ 19፥7-9፤ማር10፥4-5
24፥4 ኤር 3፥1
24፥5 ዘዳ20፥7
24፥6 ዘፀ22፥22
24፥7 ዘፀ21፥16፤ 1ቆሮ5፥13
24፥8 ዘሌ13፥1-46፤ 14፥2፤ዘዳ17፥9
24፥9 ዘኍ12፥10
24፥10 ዘፀ22፥25-27
24፥13 ዘፀ22፥26፡ 27፤ዘዳ6፥25፤ መዝ106፥31፤ዳን4፥27
24፥14 ዘሌ19፥13፤ 25፥35-43፤ ዘዳ15፥12-18፤ኢዮ24፥4፤ ምሳ14፥31፤19፥17፤ አሞ4፥1፤1ጢሞ5፥18
24፥15 ዘፀ22፥23፤ ዘሌ19፥13፤25፥35፤ ኢዮ12፥19፤ ማቴ20፥8፤ያዕ5፥4
24፥16 ዘኍ26፥11፤ ኤር31፥29-30
24፥17 ዘፀ22፥21፡ 22፤23፥2፤ዘዳ10፥18፤ ኢዮ6፥27፤24፥9፤ 29፥12፤መዝ10፥18፤ 82፥3፤ምሳ23፥10፤ ሕዝ22፥7፤
24፥18 ዘዳ15፥15
24፥19 ቍ20፤ ዘሌ19፥9፤ዘዳ10፥19፤ 14፥29፤27፥19፤ ምሳ19፥17፤28፥27፤ መክ11፥1፤ ሕዝ47፥22፤ ዘካ7፥10፤ሚል3፥5
24፥20 ዘሌ19፥10
24፥22 ቍ18
25፥1 ዘፀ21፥6፤ 23፥7፤ዘዳ1፥16-17፤ 17፥8-13፤19፥17፤ 1ነገ8፥32፤ሐሥ23፥3
25፥2 ምሳ10፥13፤ 19፥29፤ሉቃ12፥47-48
25፥3 ኤር20፥2፤ ማቴ27፥26፤ ዮሐ19፥1፤2ቆሮ11፥24
25፥4 ዘኍ22፥29፤ 1ቆሮ9፥9፤1ጢሞ5፥18
25፥5 ሩት4፥10፡

*24፥1-4፤* በሙሴ መጻሕፍት ውስጥ ፍች የተፈቀደ ሲሆን፣ ፍች ደረጃ የደረሱ ሰዎች ነገራቸውን እንዴት መጨረስ እንዳለባቸውም መመሪያ ተሰጥቶአል (ዘሌ 21፥7፡14፤ 22፥13፤ ዘኍ 30፥9 ይመ)። ኢየሱስ በተራራው ስብከቱ በ24፥1 ላይ የተሰጠውን ሕግ ገደባዊ ይዘት እንዲኖረው ከማድረጉም በላይ (ማቴ 5፥31-32) ዋናውን የሥነ ፍጥረት ሕግ ጠቅሶአል (ማቴ 19፥3-9)።

24፥5 *ደስ ያሰኛት፤* በጋብቻ ውስጥ ላለው ደስታ ከፍተኛ ግምት ተሰጥቶታል።

24፥6 *ወፍጮና መጁን፤* ለዱቄትና ለዕለት ጕርስ የሚሆነውን እህል ለመፍጨት ያገለግላል (የመሳ 9፥53 ማብ ይመ)።

24፥7 *ባሪያ ሲያደርገው፤* ከ23፥15 ጋር ያነጻጽሩ። *ክፉውን ከመካከልህ ማስወገድ፤* የ13፥5 ማብ ይመ።

24፥8 *የለምጽ ደዌን፤* የዘሌ 13፥2 ማብ ይመ።

24፥9፡18፡22 *አስታውስ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

*24፥10-13፤* የዘፀ 22፥26-27 ማብ ይመ።

24፥16 *እያንዳንዱ በራሱ ኀጢአት ይገደል፤* ሕዝ 18፥4 እና ማብ ይመ።

*24፥17-18፤* እስራኤላውያን በመከራ ውስጥ በነበሩ ጊዜ እግዚአብሔር ረድቶአቸዋል። በመሆኑም የሌሎችን መከራ ለእነርሱ መጠቀሚያ ሊያደርጉ አይገባም።

*24፥19-21፤* የዘሌ 19፥9-10 ማብ ይመ።

25፥3 *ሆኖም ግርፋቱ ከአርባ የሚበልጥ አይሁን፤* ወንጀለኛው በግርፋት ሲቀጣ ከልክ በላይ ከሆነ ከፈጸመው በደል ይበልጥ የተዋረደ ሊያደርገው ስለሚችል፣ ግርፋቱ ኢሰብአዊ እንዳይሆን ያግዳል፤ በጳውሎስ ላይ የደረሰውን ግርፋት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (2ቆሮ 11፥24)።

*25፥4፤* ይህ ሕግ ለክርስቶስ አገልጋዮችም የተሰጠ እንደ ሆነ በ1ቆሮ 9፥9-10፤ 1ጢሞ 5፥17-18 ላይ ተጠቅሶአል። *እህል እያበራየ፤* የዘፍ 50፥10፤ የሩት 1፥22 ማብ ይመ።

*25፥5-6፤* እያንዳንዱ ቤተ ሰብ የትውልድ ሐረጉ ሳይጠፋ እንዲቀጥልና መሬትም በጥቂት ቤተ ሰቦች ቍጥጥር ሥር ብቻ እንዳይሆን መከላከል፣ የሙሴ ሕግ ዐይነተኛ ባሕርይ ነው (የዘፍ 38፥8 ማብ ይመ)።

የምትወልደውም ልጅ ስሙ ከእስራኤል ፈጽሞ እንዳይጠፋ በሟች ወንድሙ ስም ይጠራ።

[7]ሆኖም ግን አንድ ሰው የወንድሙን ሚስት ለማግባት ባይፈልግ፣ ሴትዮዋ በከተማዋ በር ወዳሉት ሽማግሌዎች ሄዳ፣ "የባለቤቴ ወንድም የወንድሙን ስም በእስራኤል ለማስጠራት አልፈለገም፤ የዋርሳነት ግዴታውንም አልፈጸመልኝም" ትበላቸው። [8]ከዚያም የከተማው ሽማግሌዎች ያን ሰው ጠርተው ያነጋግሩት፤ እርሱም፣ "እርሷን ላገባት አልፈልግም" ብሎ በሐሳቡ ቢጸና፣ [9]የወንድሙም ሚስት በሽማግሌዎች ፊት ወደ እርሱ ቀርባ፣ የአንድ እግሩን ጫማ በማውለቅ በፊቱ ላይ ትትፋበትና "የወንድሙን ቤት በማይሠራ ሰው ላይ እንዲህ ያለው ድርጊት ይፈጸምበታል" ትበል። [10]የዚያም ሰው የዘር ሐረግ በእስራኤል ዘንድ፣ "ጫማው የወለቀበት ቤት" ተብሎ ይታወቃል።

[11]ሁለት ሰዎች ቢደባደቡ፣ የአንደኛው ሚስት ባሏን ከደብዳቢው እጅ ለማስጣል መጥታ፣ እጇን ዘርግታ ብልቱን ብትይዘው፣ [12]እጇን ቍረጠው፤ አትራራላት።

[13]በከረጢትህ ውስጥ ከባድና ቀላል የሆኑ ሁለት የተለያዩ ሚዛኖች አይኑሩህ። [14]በቤትህም ውስጥ ትልቅና ትንሽ የሆኑ ሁለት የተለያዩ መስፈሪያዎች አይኑሩህ። [15]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ ምድር ዕድሜህ እንዲረዝም፣ ትክክለኛና የታመነ ሚዛንና መስፈሪያ ይኑርህ። [16]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንዲህ ያሉትን ነገሮች የሚፈጽመውንና የሚያምታታውን ሁሉ ይጸየፋዋልና።

[17]ከግብፅ በወጣህ ጊዜ፣ አማሌቅ በመንገድ በአንተ ላይ ያደረገብህን አስታውስ፤ [18]ደክመህና ዝለህ በነበርህበት ጊዜ፣ በጕዞ ላይ አግኝተውህ፣ ከኋላ ያዘገሙ የነበሩትን ሁሉ ገደሉ፤ እግዚአብሔርንም (ኤሎሂም) አልፈሩም። [19]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድር ዙሪያ ካሉት ጠላቶችህ ሁሉ ባሳረፈህ ጊዜ፣ ከሰማይ በታች ያለውን የአማሌቅን መታሰቢያ ደምስስ፤ ከቶ እንዳትረሳ!

## ዐሥራትና በኵራት

**26** *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ርስት አድርጎ ወደሚሰጥህ ምድር ስትገባ፣ ስትወርሳትና ስትኖርባት፣ [2]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከሚሰጥህ ምድር ከምትሰበስበው ሰብል ሁሉ፣ በኵራት ወስደህ በቅርጫት ውስጥ አድርገው፤ ከዚያም *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለስሙ ማደሪያ እንዲሆን ወደ ሚመርጠው ስፍራ ሂድ፤ [3]በዚያም ወቅት ለሚያገለግለው ካህን፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) ለእኛ ሊሰጠን ለአባቶቻችን ወደ ማለላቸው ምድር እንደ ገባሁ ዛሬ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት እናገራለሁ" በለው። [4]ካህኑም ቅርጫቱን ከእጅህ ተቀብሎ፣ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) መሠዊያ ፊት ለፊት ያስቀምጠዋል። [5]አንተም *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት እንዲህ ብለህ ትናገራለህ፤ "አባቴ ዘላን ሶርያዊ ነበር፤ ከጥቂት ሰዎችም ጋር ወደ ግብፅ ወረደ፤ በዚያም ተቀመጠ፤ ታላቅ፣ ኀያልና ቍጥሩ የበዛ ሕዝብ ሆነ። [6]ግብፃውያን ግን ከባድ ሥራ በማሠራት አንገላቱን፤ አሠቃዩንም። [7]ከዚያ በኋላ የአባቶቻችን *አምላክ* (ያህዌ) ወደ ሆነው ወደ እግዚአብሔር (ኤሎሂም) ጮኽን፤ እግዚአብሔርም ጩኸታችንን ሰማ፤ ጕስቍልናችንን፣ ድካማችንንና የተፈጸመብንን ግፍ ተመለከተ። [8]ከዚህ የተነሣ እግዚአብሔር (ያህዌ) በብርቱ እጅና በተዘረጋች ክንድ፣ በታላቅ ድንጋጤ፣ በታምራዊ ምልክትና በድንቅ ከግብፅ አወጣን። [9]ወደዚህ ስፍራ አመጣን፤ ማርና ወተት የምታፈሰውን ይህችን ምድር ሰጠን፤ [10]አሁንም እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤ "እነሆ፣ አንተ የሰጠኸኝን የምድሪቱን በኵራት አምጥቻለሁ።" ቅርጫቱንም *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት አስቀምጠው፤ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ስገድ። [11]ከዚያም አንተ፣ ሌዋዊውና በመካከልህ የሚኖረው መጻተኛ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ለአንተና ለቤትህ በሰጠው በጎ ነገር ሁሉ ደስ ይበላችሁ።

[12]የዐሥራት ዓመት የሆነውን የሦስተኛውን ዓመት ምርት አንድ ዐሥረኛ ለይተህ ካወጣህ በኋላ በየከተሞችህ ውስጥ በልተው እንዲጠግቡ፣ ለሌዋዊው፣ ለመጻተኛው፣ አባት ለሌለውና ለመበለቲቱ ስጣቸው፣ [13]ከዚያ በኋላ *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) እንዲህ በል፤ "በሰጠኸኝ ትእዛዝ መሠረት የተቀደሰውን ክፍል ከቤቴ አውጥቼ ለሌዋዊው፣ ለመጻተኛው፣ አባት ለሌለውና ለመበለቲቱ ሰጥቻለሁ። ከትእዛዝህ አልወጣሁም፤ አንዱንም አልረሳሁም። [14]በሐዘን ላይ ሳለሁ፣ ከተቀደሰው ክፍል ላይ ምንም አልበላሁም፤ ባልነጻሁበትም ጊዜ ከዚሁ ላይ ያነሣሁትም ሆነ ለሙታን ያቀረብሁት ምንም ነገር የለም፤ *አምላኬን* እግዚአብሔርን

13፤ማቴ22፥24፤ ማር12፥19፤ ሉቃ20፥28
25፥6 ዘፍ38፥9፤ ሩት4፥5፡10
25፥7 ዘፍ23፥10፤ ሩት1፥15፤4፥1-2፡5-6
25፥9 ዘኍ12፥14፤ ኢሳ24፥22፤ሩት4፥7-8፡ 11፤ኢዮ17፥6፤ 30፥10፤ኢሳ50፥6
25፥12 ዘዳ7፥2
25፥13 ምሳ11፥1፤ 20፥23፤ሚክ6፥11
25፥15 ዘፀ20፥12
25፥16 ምሳ11፥1
25፥17 ዘፍ36፥12
25፥18 መዝ36፥1፤ ሮሜ3፥18
25፥19 ዘፍ36፥12፤ ዘፀ33፥14፤እስ9፥16፤ ዕብ3፥18-19
26፥2 ዘፀ20፥24፤ 22፥29፤ዘዳ12፥5
26፥5 ዘፍ12፥2፤ 20፥13፤25፥20፤ 34፥30፤43፥14
26፥6 ዘፀ1፥13፤ ዘኍ20፥15
26፥7 ዘፍ16፥11፤ 21፥17፤ዘፀ3፥9፤ 2ነገ13፥4፤14፥26፤ መዝ42፥9፤44፥24፤ 72፥14
26፥8 ዘኍ20፥16፤ ዘፀ3፥20፤ዘዳ4፥34፤ 34፥11-12
26፥9 ዘፀ3፥8
26፥10 ዘዳ8፥18
26፥11 ዘዳ12፥12፤ 16፥11
26፥12 ዘፍ14፥20፤ ዘኍ18፥24፤ ዘዳ14፥28-29፤ ዕብ7፥7፡9
26፥13 መዝ119፥141፡ 153፡176
26፥14 ዘሌ7፥20፤

25፥7 *አንድ ሰው የወንድሙን ሚስት ለማግባት ባይፈልግ፤* ቍ 8-10 ይመ፤ በዘፍ 38፥8-10፤ ሩት 4፥1-12 ላይ የተገለጸውንና ከዚህ ታሪክ ጋር የሚመሳሰለውን ያገናዝቡ። *በከተማዋ በር ወዳሉት ሽማግሌዎች፤* 22፥15 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 19፥1፤ የሩት 4፥1 ማብ ይመ።

*25፥11-12፤* ከዘፀ 21፥22-25 ጋር ያነጻጽሩ።

*25፥13-16፤* የዘሌ 19፥35 ማብ ይመ።

25፥14 *መስፈሪያዎች፤* የመጠን መለኪያ ነው።

25፥17 *አስታውስ፤* የ4፥10 ማብ ይመ። *አማሌቅ፤* ዘፀ 17፥8-16፤ ዘኍ 14፥45 ይመ።

25፥18 *እግዚአብሔርንም አልፈሩም፤* የዘፍ 20፥11 ማብ ይመ።

25፥19 *ባሳረፈህ ጊዜ፤* የ3፥20 ማብ ይመ።

26፥1 *ርስት፤* የዘፀ 32፥13 ማብ ይመ።

26፥2 *በኵራት፤* እዚህ ላይ የተጠቀሰው መባ አንድ ጊዜ ብቻ የሚሰጥ ሲሆን፣ በየዓመቱ ከሚቀርበው በኵራት ጋር ግን አንድ ዐይነት አይደለም (18፥4 እና ማብ ይመ)። *አምላክህ እግዚአብሔር ለስሙ ማደሪያ እንዲሆን ወደሚመርጠው ስፍራ፤* የ12፥5 ማብ ይመ።

26፥5 *ዘላን ሶርያዊ፤* ከደቡብ ከነዓን ወደ ካራን፣ ከዚያም ወደ ነበረበት አገር (ዘፍ 27-35)፣ ኋላም ወደ ግብፅ ምድር (ዘፍ 46፥3-7 ይመ) በመመለስ የባዘነውን ያዕቆብን ያመለክታል። እርሱም ሁለት የሶርያ ሴቶችን አግብቶ ነበር (ዘፍ 28፥5፤ 29፥16፡28 ይመ)። *ከጥቂት ሰዎችም ጋር ... ታላቅ ... ሕዝብ ሆነ፤* ዘፀ 1፥5፤ 1፥7 እና ማብ ይመ።

26፥11 *ደስ ይበላችሁ፤* የ12፥12 ማብ ይመ።

*26፥12፤* የ14፥22-29 ማብ ይመ።

(ያህዌ ኤሎሂም) ታዝዛለሁ፤ ያዘዝኸኝንም ሁሉ ፈጽሜአለሁ:: [15]ከቅዱስ ማደሪያህ ከሰማይ ተመልከት፤ ሕዝብህን እስራኤልንና ለአባቶ ቻችን በመሐላ ቃል በገባኸው መሠረት፣ ለእኛ የሰጠኸንን ይህችን ማርና ወተት የምታፈ ሰውን ምድር ባርክ::"

### የእግዚአብሔርን ትእዛዞች ስለ መጠበቅ

[16]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ይህን ሥርዐትና ሕግ ትጠብቅ ዘንድ ዛሬ ያዝሃል፤ አንተም በፍጹም ልብህ፣ በፍጹምም ነፍስህ ተፈ ጽመው ዘንድ ተጠንቀቅ:: [17]እግዚአብሔር *አምላክህ* (ኤሎሂም ያህዌ) እንደ ሆነ በመንገዱም እንደምትሄድ፣ ሥርዐቱን፣ ትእዛዙንና ሕጉን እንደምትጠብቅና እንደምትታዘዘው በዛሬዪቱ ዕለት ተናግረሃል:: [18]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በሰጠህ ተስፋ መሠረት አንተ፣ ሕዝቡና ርስቱ መሆንህን፣ ትእዛዙንም ሁሉ እንደምትጠብቅ በዛሬው ዕለት ተናግሮአል፤ [19]ከፈጠራቸው ሕዝቦች ሁሉ በላይ በምስጋና፣ በስም፣ በክብርም ከፍ እንደሚያ ደርግህና በሰጠውም ተስፋ መሠረት *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ቅዱስ ሕዝብ እንደም ትሆን ተናግሮአል::

### በጌባል ተራራ ላይ የቆመ መሠዊያ

**27** ሙሴና የእስራኤል አለቆች ሕዝቡን እንዲህ ብለው አዘዙ፤ "ዛሬ የማዝዛችሁን እነዚህን ትእዛዞች ሁሉ ጠብቁ፤ [2]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጥህ ምድር ለመግባት ዮርዳኖስን በተሻገራችሁ ጊዜ፣ ጥቂት ትልልቅ ድንጋዮችን አቁምና በኖራ ቅባቸው:: [3]የአባቶችህ *አምላክ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሰጠህ ተስፋ መሠረት፣ ማርና ወተት ወደምታፈስው *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ወደሚሰጥህ ምድር ለመግባት ዮርዳኖስን ስትሻገር፣ የዚህን ሕግ ቃላት ሁሉ ጻፍባቸው:: [4]ዮርዳኖስን እንደ ተሻገርህም፣ ዛሬ ባዘዝሁህ መሠረት እነዚህን ድንጋዮች በጌ ባል ተራራ ላይ ትከላቸው፤ በኖራም ቅባቸው:: [5]እዚያም *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የድ ንጋይ መሠዊያ ሥራ፤ በድንጋዮቹም ላይ ማናቸውንም የብረት መሣሪያ አታሳርፍባቸው:: [6]*የአምላክህን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) መሠዊያ ካልተጠረበ ድንጋይ ሥራ፤ በላዩም *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚቃጠል መሥዋዕት አቅርብበት:: [7]በዚያም የኅብረት መሥዋዕት* ሠዋ፤ ብላም፣ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ደስ ይበልህ:: [8]በድንጋዮቹ ላይ የዚህን ሕግ ቃላት ሁሉ ግልጽ አድርገህ ጻፍባቸው::"

### በጌባል ተራራ ላይ የተነገረ መርገም

[9]ሙሴና ሌዋውያን ካህናትም ለእስራኤል ሁሉ እንዲህ አሉ፤ "እስራኤል ሆይ፤ ጸጥ ብለህ አድምጥ! አንተ ዛሬ *የአምላክህ* የእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ሕዝብ ሆነሃል፤ [10]*አምላክህን* እግዚአ ብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ታዘዝ፤ ዛሬ የምሰጥህን ትእዛዙ ንና ሥርዐቱን ጠብቅ::"

[11]ሙሴ በዚያኑ ዕለት ሕዝቡን እንዲህ ብሎ አዘዘ:-

[12]"ዮርዳኖስን በተሻገራችሁ ጊዜ፣ ስምዖን፣ ሌዊ፣ ይሁዳ፣ ይሳኮር፣ የሴፍና ብንያም ሕዝቡን ለመባረክ በገሪዛን ተራራ ላይ ይቆሙ:: [13]ሮቤል፣ ጋድ፣ አሴር፣ ዛብሎን፣ ዳንና ንፍታሌምም በጌባል ተራራ ላይ ለመርገም ይቆሙ::

[14]ሌዋውያን ድምፃቸውን ከፍ አድርገው ለእስራኤል ሕዝብ ሁሉ እንዲህ ብለው ይናገሩ:-

[15]"የእጅ ጥበብ ባለ ሙያ የሠራውን፣ *በእግ ዚአብሔር* (ያህዌ) ዘንድ አስጸያፊ የሆነውን ምስል የሚቀርጽ ወይም ጣዖትን የሚያበጅ፣ በስውርም የሚያቆም ሰው የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[16]"አባቱን ወይም እናቱን የሚያቃልል የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[17]"የባልንጀራውን የድንበር ድንጋይ ከቦታው የሚያንቀሳቅስ የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[18]"ዐይነ ስውሩን በተሳሳተ መንገድ የሚመራ፣ የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[19]"በመጻተኛው፣ አባት በሌለውና በመበለቲቱ ላይ ፍትሕ የሚያዛባ የተረገመ ይሁን::"

*7 በትውፊት፣ *የሰላም መሥዋዕት* በመባል ይታወቃል::

ሆሴ9፥4
26፥15 ዘፀ39፥43፤ መዝ68፥5፥80፥14፤ 102፥19፤ኢሳ63፥15፤ ዘካ2፥13
26፥16 ዘዳ4፥29
26፥17 ዘፀ19፥8፤ መዝ48፥14
26፥18 ዘፀ6፥7፤ ዘዳ7፥6
26፥19 ዘዳ4፥7-8፤ 7፥6፤28፥1:13:44፤ 1ዜና14፥2፤ መዝ148፥14፤ ኢሳ40፥11፤62፥7፤ ሶፎ3፥20
27፥1 መዝ78፥7
27፥2 ዘፀ24፥4፤ ኢያ4፥1፤8፥31፤ 24፥26፤1ሳሙ7፥12
27፥3 ዘፀ3፥8
27፥4 ዘዳ11፥29
27፥5 ዘፀ20፥24:25
27፥7 ዘፀ32፥6፤ ዘዳ16፥11፤ኢያ8፥31
27፥8 ኢያ8፥32፤ ኢሳ8፥1፤30፥8፤ ዕን2፥2
27፥9 ዘዳ17፥9፤ 26፥18
27፥12 ዘፍ30፥18፤ ዘዳ11፥29፤ኢያ8፥35
27፥13 ዘዳ11፥29
27፥15 ዘፀ20፥4፤ ዘኍ5፥22፤1ነገ11፥5: 7፤2ነገ23፥13፤ ኢሳ44፥19፤66፥3፤ 1ቆሮ14፥16
27፥16 ዘፍ31፥35፤ ዘፀ21፥12፤ዘዳ5፥16
27፥17 ዘዳ19፥14
27፥18 ዘሌ19፥14
27፥19 ዘፀ22፥21፤ 23፥2፤ዘዳ10፥18፤

26፥16 *በፍጹም ልብህ፣ በፍጹም ነፍስህ፤* የ4፥29 ማብ ይመ::

*26፥17፤* ቃሉ የኪዳን ወይም የውል ቃል ሲሆን፣ እስራኤል የገባችውን መሐላ የምታድስበትን ይኸውም የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር ብቻ መሆኑንና እስራኤልም የምትገዛው ለእርሱ ብቻ እንደሆነ የሚያመለክት ነው (የዘፀ 19፥8 ማብ ይመ)::

26፥18 *ርስቱ መሆንህን፤* የዘፀ 19፥5 ማብ ይመ::

*27፥2-8፤* በጥንት የመካከለኛው ምሥራቅ አገሮች፣ የመታሰቢያ ጽሑፍ የተጻፈበት ድንጋይ ማቆም የተለመደ ነበር::

27፥2:4 *በኖራ ቅባቸው፤* በድንጋዮቹ ላይ የተቀረጸው ጽሑፍ በግልጽ እንዲታይ ለማድረግ ነው (ቍ 8 ይመ)::

27፥3:8 *የዚህን ሕግ ቃላት ሁሉ፤* ሙሴ በድጋሚ የተናገራቸው ቃላት የሚገኙበት የኪዳኑ ሕግጋት ናቸው (የዘፀ 20፥1 ማብ ይመ)::

27፥5 *የድንጋይ መሠዊያ ሥራ፤* ከመገናኛው ድንኳን መሠዊያ ጋር በቅርጽም ሆነ በአገልግሎት የተለየ ነው (የዘፀ 20፥25 ማብ ይመ)::

27፥9 *አንተ ዛሬ የአምላክህ የእግዚአብሔር ሕዝብ ሆነሃል፤* የኪዳኑን ቃል ለመጠበቅ በድጋሚ ቃል መግባታቸውን የሚያመለክት አነጋገር ነው::

27፥12 *ስምዖን ... በገሪዛን ተራራ ላይ ይቆሙ፤* ስድስቱም የያዕቆብ ዝርያዎች ሲሆኑ የተወለዱትም ከልያና ከራሔል ነው (ዘፍ 35፥23-24)፤ 11፥30 እና ማብ ይመ):: *ለመባረክ፤* ከቍ 15-26 ባለው ክፍል ላይ አንድም የበረከት ቃል አልተጠቀሰም፤ ነገር ግን የተጠቀሰው 12 የርግማን ቃል ነው (28፥15-68 ይመ):: ይሁን እንጂ በ28፥1-14 ላይ የበረከት ቃል ከመዘርዘሩም በላይ በሚገባ ተብራርቶአል::

27፥15 *ምስል የሚቀርጽ ወይም ጣዖትን የሚያበጅ፤* ከዐሥሩ ትእዛዛት መካከል አንደኛውንና ሁለተኛውን ሕግ የሚያፈርስ ማለት ነው (የዘፀ 20፥1 ማብ ይመ):: 4፥28፤ 5፥6-10፤ 31፥29፤ ኢሳ 40፥19-20፤ 41፥7፤ 44፥ 9-20፤ 45፥16፤ ኤር 10፥3-9፤ ሆሴ 8፥4-6፤ 13፥2 ይመ:: *አሜን፤* ለማለት ያህል የሚባል ሳይሆን፣ ሕዝቡ ኪዳኑን ተቀብሎ ቢጠብቅ በረከት እንደሚያገኝ ባይጠብቅ ግን ርግማኑ እንደሚደርስበት ከልብ መስማማቱን የሚያረጋግጥበት ቃል ነው (ቍ16-26 ይመ)::

*27፥16፤* 5፥16፤ ዘፀ 20፥12 እና ማብ ይመ::

*27፥17፤* የ19፥14 ማብ ይመ::

*27፥19፤* 24፥17-18 እና ማብ ይመ::

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[20]"ከአባቱ ሚስት ጋር የሚተኛ የተረገመ ይሁን፤ የአባቱን መኝታ ያረክሳልና::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[21]"ከማናቸውም እንስሳ ጋር የግብረ ሥጋ ግንኙነት የሚያደርግ የተረገመ ይሁን::

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[22]"የአባቱ ወይም የእናቱ ልጅ ከሆነችው እኅቱ ጋር የግብረ ሥጋ ግንኙነት የሚፈጽም የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[23]"ከዐማቱ ጋር የግብረ ሥጋ ግንኙነት የሚፈጽም የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[24]"ባልንጀራውን በድብቅ የሚገድል የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[25]"ንጹሕን ሰው ለመግደል ጉቦ የሚቀበል የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

[26]"የዚህን ሕግ ቃሎች በመፈጸም የማይጸና የተረገመ ይሁን::"

ሕዝቡም ሁሉ፣ "አሜን!" ይበል::

## በመታዘዝ የሚገኝ በረከት

**28** *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በፍጹም ብትታዘዝና እኔ ዛሬ የምሰጥህን ትእዛዙን ሁሉ በጥንቃቄ ብትከተል፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በምድር ላይ ከሚኖሩ አሕዛብ ሁሉ በላይ ከፍ ያደርግሃል:: [2]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ብትታዘዝ፣ እነዚህ በረከቶች ሁሉ ያንተ ይሆናሉ፤ አይለዩህምም::

[3]በከተማ ትባረካለህ፣ በዕርሻህም ትባረካለህ::

[4]የማሕፀንህ ፍሬ፣ የምድርህ አዝመራ፣ የእንስሳትህ ግልገሎች፣ የከብትህ ጥጃ፣ የበግና የፍየል ግልገሎችህም ይባረካሉ::

[5]እንቅብህና ቡሖ ቃህ ይባረካሉ::

[6]ስትገባ ትባረካለህ፤ ስትወጣም ትባረካለህ::

[7]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በአንተ ላይ የሚነሡ ጠላቶችህን በፊትህ እንዲሸነፉ ያደርጋቸዋል፤ በአንድ አቅጣጫ ይመጡብሃል፤ በሰባት አቅጣጫም ከአንተ ይሸሻሉ::

[8]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በጐተራህና እጅህ በነካው ሁሉ በረከቱን ይልካል:: *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህም ምድር ላይ ይባርክሃል::

[9]*የአምላክህን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዞች የምትጠብቅና በመንገዱ የምትሄድ ከሆነ፣ በመሐላ በሰጠህ ተስፋ መሠረት የተቀደሰ ሕዝቡ አድርጎ ያቆምሃል፤ [10]ከዚያም የምድር አሕዛብ ሁሉ *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ስም መጠራትህን ያያሉ፤ ይፈሩሃልም:: [11]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሊሰጥህ ለአባቶችህ በማለላቸው ምድር በማሕፀንህ ፍሬ፣ በእንስሳትህም ግልገል፣ በምድርህም ሰብል የተትረፈረፈ ብልጽግና ይሰጥሃል::

[12]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለምድርህ በወቅቱ ዝናብን ለማስጠትና የእጅህን ሥራ ሁሉ ለመባረክ፣ መልካሙን መዝገብ ሰማዩን ይከፍትልሃል፤ አንተም ለብዙ አሕዛብ ታበድራለህ እንጂ ከአንዳቸውም አትበደርም:: [13]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ራስ እንጂ ጅራት አያደርግህም:: ዛሬ የምሰጥህን *የአምላክህን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ትእዛዝ በጥንቃቄ ብትጠብቅ መቼውንም ቢሆን እላይ እንጂ ፈጽሞ እታች አትሆንም:: [14]ሌሎችን አማልክት በመከተል እነርሱን በማገልገል ዛሬ ከምሰጥህ ትእዛዞች ቀኝም ግራም አትበል::

## አለመታዘዝ የሚያስከትላቸው ርግማኖች

[15]ነገር ግን *ለአምላክህ* ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ባትታዘዝ በዛሬዋ ዕለት የምሰጥህን ትእዛዙንና ሥርዐቱን ሁሉ በጥንቃቄ ባትከተላቸው፣ እነዚህ ርግማኖች ሁሉ ይደርሱብሃል፤ ያጥለቀልቁሃልም:-

[16]በከተማ ትረገማለህ፤ በዕርሻም ትረገማለህ::

[17]እንቅብህና ቡሖ ቃህ የተረገሙ ይሆናሉ::

[18]የማሕፀንህ ፍሬ፣ የዕርሻህ ሰብል፣ የመንጋህ ጥጆች፣ የበግና የፍየል ግልገሎችህ ይረገማሉ::

[19]ስትገባ ትረገማለህ፤ ስትወጣም ትረገማለህ::

[20]እርሱን[T] በመተው ክፉ ድርጊት ከመፈጸምህ የተነሣ፣ እስክትደመሰስ ፈጥነህም እስክትጠፋ ድረስ እጅህ በነካው ሁሉ ላይ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ርግማንን፣ መደናገርንና ተግሣጽን ይሰድብሃል:: [21]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ልትወርሳት ከምትገባበት ምድር ላይ እስኪያጠፋህ ድረስም፣ በደዌ ይቀሥፍሃል:: [22]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እስክትጠፋ ድረስ በሚቀሥፍ ደዌ፣ ትኩሳትና ዕባጭ፣ ኀይለኛ ሙቀትና ድርቅ፣ ዋግና አረማሞ ይመታሃል:: [23]ከራስህ በላይ ያለው ሰማይ ናስ፣ ከእግርህ በታች ያለው ምድርም ብረት

24፥19
27፥20 ዘፍ34፥5፤ ዘሌ18፥7
27፥21 ዘፀ22፥19
27፥22 ዘሌ18፥9
27፥23 ዘሌ20፥14
27፥24 ዘፍ4፥23፤ ዘፀ21፥12
27፥25 ዘፀ23፥7-8፤ ዘሌ19፥16
27፥26 ዘሌ26፥14፤ ዘዳ28፥15፤ መዝ119፥21፤ ኤር11፥3:5፤ገላ3፥10
28፥1 ዘሌ26፥3፤ ዘኍ24፥7፤ዘዳ15፥5፤ 26፥19
28፥2 ኤር32፥24፤ ዘካ1፥6
28፥3 ዘፍ39፥5፤ መዝ144፥15
28፥4 ዘፍ49፥25፤ ዘዳ8፥18
28፥6 መዝ121፥8
28፥7 ዘሌ26፥8: 17፤2ዜና6፥34፤
28፥8 ዘዳ15፥4
28፥9 ዘፀ19፥6፤ ዘሌ26፥3
28፥10 ዘኍ6፥27፤ 1ነገ8፥43፤ኤር25፥29፤ ዳን9፥18
28፥11 ቊ4፤ ዘፍ30፥27፤ዘዳ30፥9
28፥12 ቊ44፤ ዘሌ25፥19፤26፥4፤ ዘዳ15፥3:6፤ 1ነገ8፥35-36፤18፥1፤ ኢዮ38፥22፤ መዝ65፥11፤68፥10፤ 104፥13፤135፥7፤ ኢሳ5፥6፤30፥23፤ 32፥20፤61፥9፤65፥23፤ ኤር10፥13፤31፥12፤ 32፥38-41፤51፥16፤ ሕዝ34፥26፤ሚል3፥12
28፥13 ዘዳ26፥19፤ ኤር11፥6
28፥14 ዘዳ5፥32፤ ኢሱ1፥7
28፥15 ዘዳ27፥26፤ 29፥27፤ኢሱ23፥15፤ 1ነገ9፥6፤2ዜና7፥19፤ ኤር12፥5፤ዳን9፥11፤ ሚል2፥2
28፥16 ቊ3
28፥17 ቊ5
28፥18 ቊ4
28፥19 ቊ6
28፥20 ቊ8:15፤ ዘፀ32፥22፤ዘሌ26፥16፤ ዘዳ4፥26፤መዝ39፥11፤ 76፥6፤80፥16፤ 54፥9፤66፥15፤ ኤር42፥18፤ሕዝ5፥25፤ ሚል2፥2፤3፥9፤4፥6
28፥21 ዘሌ2625፤ ዘኍ14፥12፤ኤር24፥10፤28፥26 ዘፍ40፥19፤ መዝ79፥2፤ኢሳ18፥6፤ ኤር7፥33፤12፥9፤ 15፥2፤16፥4፤19፥7፤34፥20 አሞ4፥10 28፥22 ቊ48፤ ዘሌ26፥16:25፤ ዘዳ4፥26፤32፥24፤ 2ነገ8፥1፤ኢዮ12፥15፤ መዝ105፥16፤ ኤር2፥17፤14፥1፤ አሞ4፥9፤ ሐጌ1፥11፤ሚል3፥9 28፥23 ዘሌ26፥19

*27፥20፤* ከ22፥30 ጋር ያነጻጽሩ፤ ዘሌ 18፥8 ይመ::

*27፥21፤* ዘፀ 22፥19 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዘሌ 18፥23፤ 20፥15-16 ይመ::

*27፥22፤* ዘሌ 18፥9 ይመ::

*27፥23፤* ዘሌ 18፥8 ይመ::

*27፥24-25፤* 5፥17፤ ዘፀ 20፥13፤ 21፥12፤ ዘሌ 24፥17:21 ይመ::

*27፥26፤* ማንም ሰው የእግዚአብሔርን ሕግ ሙሉ በሙሉ መጠበቅ ስለማይችል፣ ሰዎች ሁሉ ከርግማን በታች መሆናቸውን ለማረጋገጥ በገላ 3፥10 ላይ ተጠቅሶአል:: *በመፈጸም፤* ከሕጉ ወገን ነኝ ብሎ በመናገር ከለላን ለማግኘት መሞከር በራሱ በቂ አይደለም፤ በሕጉ መሠረት መኖር አስፈላጊ ነው::

*28፥1-14፤* እነዚህ በረከቶች በቊ 15-44 ላይ የተጠቀሱት ርግማኖች ተቃራኒ ናቸው (በተለይ ከቊ 3-6 ያለውን ከቊ 16-19 ጋር ያነጻጽሩ)::

28፥5:17 *እንቅብህና ቡሖ ቃህ፤* በቤት ውስጥ ለእህል ማከማቻና ለምግብ ማዘጋጃ የሚያገለግሉ ናቸው::

*28፥7፤* የዚህን ተቃራኒ በቊ 25 ላይ ይመ::

28፥12 *መልካሙን መዝገብ ሰማዩን፤* ሰማያት የዝናብ፣ የበረዶ፣ የበረዶ ድንጋይና የነፋስ መመንጫ መሆናቸውን በኢዮ 38፥22፤ መዝ 135፥7፤ ኤር 10፥13፤ 51፥16 ይመ:: *ታበድራለህ፤* የዚህን ተቃራኒ በቊ 44፤ እንዲሁም በ15፥6 ማብ ላይ ይመ::

28፥13 *ራስ እንጂ ጭራ አያደርግህም፤* የዚህን ተቃራኒ በቊ 44 ላይ ይመ::

28፥23 *ሰማይ፣ ናስ ... ምድርም ብረት፤* ሰማይን በስቶ የሚወርድ፣ ምድርን ዘልቆ የሚገባ ዝናብ አይኖርም ለማለት ነው::

ይሆናል። [24]እግዚአብሔር (ያህዌ) የምድርህን ዝናብ ወደ ዐቧራነትና ወደ ትቢያነት ይለውጠዋል፤ ይህም እስክትጠፋ ድረስ ከሰማይ ይወርድብሃል።

[25]እግዚአብሔር (ያህዌ) በጠላቶችህ ፊት እንድትሸነፍ ያደርግሃል፤ በአንድ አቅጣጫ ትመጣባቸዋለህ፤ ነገር ግን በሰባት አቅጣጫ ከፊታቸው ትሸሻለህ፤ ለምድር መንግሥታትም ሁሉ መሸማቀቂያ ትሆናለህ። [26]ሬሳህ የሰማይ አሞሮችና የምድር አራዊት ሲሳይ ይሆናል፤ በማስፈራራትም የሚያባርራቸው አይኖርም። [27]እግዚአብሔር (ያህዌ) በማትድንበት በግብፅ ብጉንጅ፣ በእባጭ፣ በሚመግል ቊስልና በዕከክ ያሠቃይሃል። [28]እግዚአብሔር (ያህዌ) በእብደት በዕውርነትና ግራ በማጋባት ያስጨንቅሃል። [29]በእኩለ ቀን፣ በጨለማ እንዳለ ዕውር በዳበሳ ትሄዳለህ። የምታደርገው ሁሉ አይሳካልህም። በየዕለቱ ትጨቈናለህ፤ ትመዘበራለህም፤ የሚታደግህ አይኖርም።

[30]ሚስት ለማግባት ልጃገረድ ታጫለህ፤ ሌላው ግን ወስዶ ይደፍራታል። ቤት ትሠራለህ፣ ግን አትኖርበትም። ወይን ትተክላለህ፤ ፍሬውን ግን አትበላም። [31]በሬህ ዐይንህ እያየ ይታረዳል፤ ከሥጋውም አንዳች አትቀምስም። አህያህም በግድ ይወሰድብሃል፤ አይመለስልህም። በጎችህ ለጠላቶችህ ይሰጣሉ፤ የሚያስጥላቸውም አይኖርም። [32]ወንዶችና ሴቶች ልጆችህ ለባዕድ ሕዝብ ይሰጣሉ፤ እጅህንም ለማንሣት ዐቅም ታጣለህ፤ ከዛሬ ነገ ይመጣሉ፤ በማለትም ዐይኖችህ ሁልጊዜ እነርሱን በመጠባበቅ ይደክማሉ። [33]የምድርህንና የድካምህን ፍሬ ሁሉ የማታውቀው ሕዝብ ይበላዋል፤ ዕድሜ ልክህን በጭካኔና በጭቈና ከመኖር በቀር የሚተርፍህ ነገር አይኖርም። [34]የምታየው ሁሉ ያሳብድሃል። [35]እግዚአብሔር (ያህዌ) ከእግርህ ጥፍር እስከ ራስህ ጠጕር በሚዛመት፣ ሊድን በማይችልና በሚያሠቃይ ቊስል ጒልበትህንና እግርህን ይመታሃል።

[36]እግዚአብሔር (ያህዌ) አንተንና በላይህ ያነገሥኸውን ንጉሥ፣ አንተና አባቶችህ ወደ ማታውቀት ሕዝብ ይወስዳችኋል፤ ከዚያም ከዕንጨትና ከድንጋይ የተሠሩ ሌሎች አማልክትን ታመልካለህ። [37]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንድትገባ በሚያደርግበት ምድር ለሕዝብ ሁሉ መሸማቀቂያ፣ ማላገጫና መዘባበቻ ትሆናለህ።

[38]በዕርሻ ላይ ብዙ ዘር ትዘራለህ፤ አንበጣ ስለሚበላው የምትሰበስበው ጥቂት ይሆናል። [39]ወይን ትተክላለህ፤ ትንከባከበዋለህ፤ ነገር ግን ዘለላውን አትሰበስብም። [40]በአገርህ ምድር ሁሉ የወይራ ዛፍ ይኖርሃል፤ ፍሬው ስለሚረግፍብህ ግን ዘይቱን አትጠቀምበትም። [41]ወንዶችና ሴቶች ልጆች ትወልዳለህ፤ ነገር ግን በምርኮ ስለሚወሰዱ፣ አብረውህ አይኖሩም። [42]ዛፍህንና የምድርህን ሰብል ሁሉ የአንበጣ መንጋ ይወርሰዋል።

[43]በመካከልህ የሚኖር መጻተኛ ከአንተ በላይ ከፍ ከፍ ሲል አንተ ግን ዝቅ ዝቅ ትላለህ። [44]እርሱ ያበድርሃል እንጂ አንተ አታበድረውም። እርሱ ራስ ይሆናል፤ አንተ ግን ጅራት ትሆናለህ።

[45]እነዚህ ርግማኖች ሁሉ በአንተ ላይ ይመጣሉ፤ አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ስላልታዘዝህና የሰጠህን ትእዛዝና ሥርዐት ስላልጠበቅህ እስክትጠፋ ድረስ ይከተሉሃል፤ ይወርዱብሃልም። [46]ለአንተና ለዘርህ ለዘላለም ምልክትና መገረም ይሆናሉ። [47]በብልጽግና ጊዜ አምላክህን እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) በደስታና በሐሤት ስላላገለገልኸው፣ [48]በራብና በጥም፣ በእርዛትና በከፋ ድኽነት እግዚአብሔር (ያህዌ) የሚያስነሣብህን ጠላቶችህን ታገለግላለህ፤ እስኪያጠፉህም ድረስ በዐንገትህ ላይ የብረት ቀንበር ይጭንብሃል።

[49]እግዚአብሔር (ያህዌ) እንደ ንስር ፈጥኖ የሚወርድንና ቋንቋውን የማታውቀውን ሕዝብ እጅግ ሩቅ ከሆነ፣ ከምድርም ዳርቻ ያስነሣብሃል፤ [50]ሽማግሌ የማያከብር፣ ለብላቴና የማይራራ፣ ሲያዩት የሚያስፈራ ሕዝብ ነው። [51]እስክትጠፋም ድረስ የእንስሶችህን ግልገልና የምድርህን ሰብል ይበላል፤ እስኪያጠፉህም ድረስ እህል፣ አዲስ የወይን ጠጅ ሆነ ዘይት፣ የመንጋህን ጥጃ ሆነ፣ የበግና ፍየል መንጋህን ግልገል አያስቀርልህም። [52]የምትታመንባቸውን ታላላቅ የተመሸጉ ቅጥሮች እስኪወድቁ ድረስ በመላው አገርህ ያሉትን ከተሞችህን ሁሉ ይከባል፤ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በሚሰጥህ ምድር ያሉትን ከተሞች በሙሉ ይወራቸዋል።

[53]ጠላቶችህ ከበው በሚያስጨንቁህ ጊዜ፣ ከሥቃይ የተነሣ፣ አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሰጠህን፣ የወገብህ ፍሬ የሆኑትን

ኢሳ17፥13፤51፥20፤
28፥24 ዘሌ26፥19፤ ዘዳ11፥17፤1ነገ8፥35፤17፥1፤ኢሳ5፥6፤ ኤር14፥1፤ሐጌ1፥10
28፥25 ቍ37፤ ዘሌ26፥17፤ 1ሳሙ4፥10፤2ዜና29፥8፤30፥7፤ መዝ78፥62፤ ኤር15፥4፤24፥9፤26፥6፤29፥18፤44፥12፤ ሕዝ23፥46
28፥27 ዘዳ7፥15
28፥29 ዘፍ19፥11፤ ዘፀ10፥21፤መሳ3፥9፤ ኢዮ4፥14፤2ነገ13፥5፤ ኢዮ5፥14፤12፥25፤ 24፥13፤38፥15፤ ኢሳ59፥10፤ ኢሳ19፥20፤43፥11፤ ሆሴ13፥4፤አብ1፥21
28፥30 ኢዮ31፥10፤ ኢሳ65፥22፤ኤር12፥13፤ አሞ5፥11
28፥32 ቍ41
28፥33 ኤር5፥15-17፤ 6፥6፤22፥17፤ሕዝ25፥4
28፥34 ቍ67
28፥35 ዘዳ7፥15፤ ኢዮ2፥7፤7፥5፤13፥28፤ 30፥17፤30፤ኢሳ1፥6፤ ራእ16፥2
28፥36 ዘዳ4፥27፤28፤ 1ሳሙ12፥25፤ 2ነገ24፥14፤25፥7፤11፤ 2ዜና33፥11፤36፥21፤ ዕዝ5፥12፤ኤር15፥14፤ 16፥13፤27፥20፤39፥1-9፤ 52፥28፤ሰቆ1፥3
28፥37 ቍ25፤ 1ነገ9፥7፤2ዜና7፥20፤ ዕዝ9፥7፤መዝ22፥7፤ 39፥8፤44፥13፤14፤ 64፥8፤ኤር18፥16፤ 19፥8፤24፥9፤25፥9፤ 18፤29፥18፤42፥18፤ 44፥8፤48፥27፤ ሰቆ2፥15፤ ሕዝ5፥15፤ሚክ6፥16
28፥38 ዘፀ10፥4፤15፤ ዘሌ26፥20፤ መዝ129፥7፤ ኢሳ5፥10፤ኤር12፥13፤ ሆሴ8፥7፤ሐጌ1፥6፤ 9፤2፥16፤ ሚክ6፥15
28፥39 ዘሌ10፥9፤ ኢሳ5፥10፤17፥10-11፤ ኢዩ1፥4፤2፥25፤ ሶፎ1፥13፤ሚል3፥11
28፥40 ኤር11፥16፤ ሚክ6፥15
28፥41 ቍ32
28፥42 ቍ12፥38፤ ዘጸ26፥19፤መሳ6፥5፤ 7፥12፤ኤር46፥23
28፥43 ቍ13
28፥44 ቍ12፤

28፥45 ቍ15፤ ዘፀ15፥9፤ዘዳ4፥25-26 28፥46 ዘኍ16፥38፤ መዝ71፥7፤ኢሳ8፥18፤20፥3፤ሕዝ5፥15፤ዘካ3፥8 28፥47 ዘሌ23፥40፤ ዘዳ10፥12፤ነህ9፥35 28፥48 ዘፍ49፥8፤ ኤር14፥3፤28፥13-14፤ ሰቆ1፥14፤4፥4 28፥49 ዘፍ11፥7፤ ዘሌ26፥44፤2ሳሙ1፥23፤ኢሳ5፥26-30፤ 7፥18-20፤39፥3፤ኤር4፥13፤16፤5፥15፤6፥22፤25፥32፤31፥8፤48፥40፤ 49፥22፤ ሰቆ4፥19፤ሕዝ17፥3፤ ሆሴ8፥1፤1ቆሮ14፥21፤ዕብ1፥6 28፥50 ኢሳ47፥6 28፥51 ቍ33፤ዘኍ18፥12፤መሳ6፥4፤መዝ4፥7፤ ኢሳ36፥17፤ሐጌ1፥11 28፥52 2ነገ6፥24፤ ኤር10፥18፤ሕዝ6፥10፤ ሶፎ1፥14-16፡17 28፥53 ቍ57፤ ዘሌ26፥29፤2ነገ6፥28-29፤ ሰቆ2፥20

[†20] ዕብራይስጡ፣ እኔን ይላል።

*28፥25፤ የዚህን ተቃራኒ በቍ7 ላይ ይመ።*
28፥27 *በግብፅ ብጉንጅ፤* የዘፀ 9፥9 *ማብ ይመ።*
*28፥30፤* 20፥5-7 *ይመ።*
*28፥35፤* የዘፀ 9፥11 *ማብ ይመ።*
*28፥44፤* የቍ 12-13 *ማብ ይመ።*
28፥49 *እንደ ንስር ፈጥኖ የሚወርደውን፤* የአሦራውያንን (ሆሴ 8፥1 ይመ) እንዲሁም የባቢሎናውያንን ፈጣንነትና ኀያልነት የሚያመለክት ተምሳሌታዊ አነጋገር ነው (ኤር 48፥40፤49፥22 ይመ)። *ቋንቋውን የማታውቀውን ሕዝብ፤* የአሦራውያንና የባቢሎናውያን ቋንቋ ከዕብራይስጥ ቋንቋ ጋር ዝምድና ያለው ቢሆንም፣ አብዛኛው እስራኤላዊ ግን እነዚህን ቋንቋዎች መረዳት አይችልም ነበር (ኢሳ 28፥11፤ 33፥19 እና ማብ፤ 1ቆሮ 14፥21 ይመ)። *ከምድር ዳርቻ፤* 'ከሩቅ ምድር' ለማለት ሲሆን፣ ይህም ወሰን ዳርቻው የማይታወቀውን ክልል የሚያመለክት ተምሳሌታዊ አገላለጽ ነው፤ ይህም የምድርን አድማስ ይዞ በጊዜው ይታወቅ የነበረውን ዓለም የሚያካልል ለማለት ነው።

28፥53 *ጠላቶችህ ከበው በሚያስጨንቁህ ጊዜ፤* ቍ 55፡57 ይመ፤ ይህ ሐረግ ተደጋግሞ የተጠቀሰው፣ እስራኤላውያን እግዚአብሔርን ባይታዘዙ የሚደርስባቸውን መከራ በአጽንዖት ለመግለጽ ነው። *የወንዶችና የሴቶች ልጆችህን ሥጋ ትበላለህ፤* ይህ ርግማን መድረሱን በ2ነገ 6፥24-29፤ በሰቆ 2፥20፤ 4፥10 ላይ ይመ።

የወንዶችና የሴቶች ልጆችህን ሥጋ ትበላለህ። [54]ሌላው ይቅርና በመካከልህ በጣም ደግና ርኅሩኅ የሆነው ሰው እንኳ ለገዛ ወንድሙ ወይም ለሚወዳት ሚስቱ ወይም ለተረፉት ልጆቹ አይራራላቸውም። [55]ከሚበላው ከልጆቹ ሥጋ ላይም ቅንጣት ታህል እንኳ ከእነርሱ ለአንዱ አያቀምስም፤ ከተሞችህ ሁሉ በመከበባቸው ጠላቶችህ ከሚያደርሱብህ ሥቃይ የተነሣ ለእርሱ የቀረለት ይህ ብቻ ነውና። [56]በመካከልህ ተለሳልሳና ተቀማጥላ የምትኖር፣ ከልስላሴና ከቅምጥልነት የተነሣ፣ እግሯን ዐፈር ነክቶት የማያውቅ ሴት፣ የምትወደውን ባሏን፣ የገዛ ወንድ ወይም ሴት ልጆቿን ትንቃለች። [57]ከማሕፀኗ የወጣውን እንግዴ ልጇንና የምትወልዳቸውን ሕፃናት ትጠየፋለች፤ ይህን የምታደርገውም በመከራው ወቅት ጠላቶችህ ከተሞችህን ከበው በሚያስጨንቁህ ጊዜ፣ እነርሱን ደብቃ ለመብላት ስትል ነው።

[58]በዚህ መጽሐፍ የተጻፈውን የዚህን ሕግ ቃሎች በጥንቃቄ ባትከተልና አስደናቂና አስፈሪ የሆነውን *የአምላክህን* የእግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ስም ባታከብር፣ [59]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) አስፈሪ መቅሠፍት፣ አስጨናቂና ለብዙ ጊዜ የሚቈይ መዓት፣ አሠቃቂና በቀላሉ የማይወገድ ደዌ በአንተና በዘሮችህ ላይ ይልክባችኋል። [60]የምትፈራቸውንም የግብፅ በሽታዎች ሁሉ ያመጣብሃል፤ በአንተም ላይ ይጣበቃሉ። [61]ደግሞም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በዚህ የሕግ መጽሐፍ ያልተጻፈውን ማንኛውንም ዐይነት ደዌና መከራ እስክትጠፋ ድረስ ያመጣብሃል። [62]ለአምላካችሁ ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ስላልታዘዛችሁ፣ እንደ ሰማይ ከዋክብት በዝታችሁ የነበራችሁት እናንተ ጥቂት ብቻ ትቀራላችሁ። [63]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እናንተን በማበልጸግና ቍጥራችሁን በማብዛት ደስ እንደተሰኘ፣ እናንተን በማጥፋትና በመደምሰስም ደስ ይለዋል፤ ልትወርሷት ከምትገቡባት ምድር ትነቀላላችሁ።

[64]ከዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ከአንዱ የምድር ዳርቻ እስከ ሌላው ዳርቻ በሕዝቦች ሁሉ መካከል ይበትንሃል። በዚያ አንተም ሆንህ አባቶችህ የማታውቋቸውን ከዕንጨትና ከድንጋይ የተሠሩ ሌሎች አማልክትን ታመልካለህ። [65]በእነዚያ ሕዝቦች መካከል ዕረፍት አታገኝም፤ ለእግርህም ጫማ ማረፊያ ቦታ አይኖርም። እዚያም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚጨነቅ አእምሮ፣ በናፍቆት የሚደክም ዐይንና ተስፋ የሚቈርጥ ልብ ይሰጥሃል። [66]ቀንም ሆነ ሌሊት በፍርሀት እንደ ተዋጥህ፣ ሕይወትህ ዋስትና ሳታገኝ፣ ዘወትር በሥጋት ትኖራለህ። [67]ልብህ በፍርሀት ከመሞላቱና ዐይንህ ከሚያየው የተነሣ፣ ሲነጋ፣ "ምነው አሁን በመሸ!" ሲመሽ ደግሞ፣ "ምነው አሁን በነጋ!" ትላለህ። [68]*ዳግመኛ አትመለስበትም* ባልሁህ መንገድም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በመርከብ ወደ ግብፅ ይመልስሃል። እዚያም ወንዶችና ሴቶች ባሮች እንድትሆኗቸው ለጠላቶቻችሁ ለመሸጥ ራሳችሁን ታቀርባላችሁ፤ የሚገዛችሁ ግን አይኖርም።

## የቃል ኪዳኑ መታደስ

**29** *እግዚአብሔር* (ያህዌ) በኮሬብ ከገባው ቃል ኪዳን በተጨማሪ በሞዓብ ምድር ከእስራኤላውያን ጋር እንዲያደርግ ሙሴን ያዘዘው የኪዳኑ ቃሎች እነዚህ ናቸው።

[2]ሙሴ እስራኤላውያንን ሁሉ ጠርቶ እንዲህ አላቸው፦ "*እግዚአብሔር* (ያህዌ) በግብፅ፣ በፈርዖን፣ በሹማምንቱ ሁሉና በመላ አገሩ ላይ ያደረገውን ሁሉ ዐይኖቻችሁ አይተዋል። [3]እነዚያን ከባድ ፈተናዎች፣ ታምራዊ ምልክቶችና ታላላቅ ድንቆች በገዛ ዐይኖቻችሁ አይታችኋል። [4]ነገር ግን እስከ ዛሬ ድረስ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) የሚያስተውል አእምሮ ወይም የሚያይ ዐይን ወይም የሚሰማ ጆሮ አልሰጣችሁም። [5]በምድረ በዳ በመራኋችሁ በእነዚያ አርባ ዓመታት ውስጥ ልብሳችሁ አላረጀም፤ የእግራችሁም ጫማ አላለቀም። [6]ቂጣ አልበላችሁም፤ የወይን ጠጅ ወይም ሌላ የሚያሰክር መጠጥ አልጠጣችሁም፤ ይህን ያደረግሁት እኔ *እግዚአብሔር* አምላካችሁ (ያህዌ ኤሎሂም) እንደ ሆንሁ ታውቁ ዘንድ ነው።

[7]ወደዚህ ስፍራ በደረሳችሁ ጊዜ፣ የሐሴቦን ንጉሥ ሴዎንና የባሳን ንጉሥ ዐግ ሊወጉን

ዘጸ26፥19
28፥55 2ነገ6፥29
28፥56 ኢሳ47፥1፤ ሰቆ4፥10
28፥57 ቍ53
28፥58 ዘፀ3፥15፤ ዘዳ31፥24፤መዝ96፥4፤ ኤር5፥22፤ሚል1፥14፤ 2፥5፤3፥5፡16፤4፥2፤ ኢሱ7፥9
28፥60 ዘፀ15፥26
28፥61 ዘዳ4፥25-26፤29፥21፤30፥10፤ 31፥26፤ኢሱ1፥8፤ 8፥34፤23፥6፤24፥26፤ 2ነገ14፥6፤22፥8፤ 2ዜና17፥9፤25፥4፤ ነህ8፥1፡18፤ሚል4፥4
28፥62 ዘፍ22፥17፤ ዘሌ26፥22፤ዘዳ4፥27፤ 10፥22
28፥63 ዘፍ6፥7፤ ዘዳ30፥9፤መዝ52፥5፤ ምሳ1፥26፤ኢሳ62፥5፤ 65፥19፤ኤር12፥14፤ 31፥28፤32፥41፤45፥4፤ ሶፎ3፥17
28፥64 ዘዳ4፥27፡ 32፤11፥28፤32፥17፤ ዕዝ9፥7፤ነህ1፥8፤ መዝ44፥11፤ኢሳ6፥12፤ ኤር8፥19፤13፥24 ፤18፥17፤22፥22፤ 32፥23፤43፥11፤ 52፥27
28፥65 ዘሌ26፥16፡ 36፤ሰቆ1፥3፤ ኢዩ11፥20፤ሆሴ9፥17
28፥67 ቍ34
28፥68 ዘፀ13፥14
29፥1 ዘፀ3፥1፤ ዘሌ7፥38
29፥2 ዘፀ19፥4
29፥3 ዘዳ4፥34
29፥4 ኢሳ6፥10፤ 32፥3፤48፥8፤ ኤር5፥21፤ሕዝ12፥2፤ ማቴ13፥15፤ኤፌ4፥18፤ ሮሜ11፥8
29፥5 ዘዳ8፥2፡4
29፥6 ዘሌ10፥9፤ ዘዳ8፥3
29፥7 ዘኍ21፥21-24፤ 25፤26፤33-35፤

28፥58 *የዚህን ሕግ ቃሎች፤* የ31፥24 ማብ ይመ። *አስደናቂና አስፈሪ የሆነውን የአምላክህን የእግዚአብሔርን ስም ባታከብር፤* የዘፀ 3፥15 ማብ ይመ። በብሉይ ኪዳን ለእግዚአብሔር መጠሪያ የሆነው ስም ትክክለኛ አነባበብ እንዴት እንደሆነ አይታወቅም፤ የዕብራይስጡ ቃል ያለ አናባቢ ፊደሎች የተጻፈ በመሆኑ የስሙን ትክክለኛ አነባበብ ማወቅ አልተቻለም፤ ይህም በታሪክና እግዚአብሔር ለሕዝቡ በሰጠው መገለጥ ውስጥ ከምናገኛቸው አስገራሚ ነገሮች መካከል አንዱ ነው (የዘፍ 2፥4 ማብ ይመ)። ያም ሆነ ይህ ለእግዚአብሔር መጠሪያ የሆነው ስም፣ "ያህዌ" የሚለው ሳይሆን አይቀርም። የኋላ ኋላ ይህ ስም በአይሁዳውያን ዘንድ እጅግ የተቀደሰ ተደርጎ ስለሚቈጠር ስሙን መጥራት ጨርሶ ቀርቶ ነበር፤ ይህም የሆነው በዘፀ 20፥7 እና በዘሌ 24፥16 ላይ የተጠቀሰውን ትእዛዝ እንተላለፋለን የሚል ፍራቻ ስላደረባቸው ነው። በዚህ የአማርኛ ትርጉም ውስጥ ይህ ስም፣ "እግዚአብሔር" ተብሎ ተተርጕሞአል።

28፥60 *የግብፅ በሽታዎች፤* በግብፅ ምድር መቅሠፍት በወረደ ጊዜ የታዩትን የበሽታ ዐይነቶች ማለት ነው (7፥15፤ ዘፀ 15፥26 ይመ)።

28፥61 *የሕግ መጽሐፍ፤* የ31፥24 ማብ ይመ።

28፥62 *እንደ ሰማይ ከዋክብት፤* 1፥10 ይመ። እንዲሁም የዘፍ 13፥16፤ 15፥5 ማብ ይመ።

28፥64 *ይበትንሃል፤* እስራኤላውያን ወደ አሦርና (722-721 ዓ.ቅ.ክ)፤ ወደ ባቢሎን ምድር (586 ዓ.ቅ.ክ) ተማርከው በተወሰዱ ጊዜ ይህ ቃል ተፈጽሞአል (2ነገ 17፥6፤ 25፥21 ይመ)።

28፥68 *ዳግመኛ አትመለስበትም ባልሁህ መንገድም፤* 17፥16፤ ዘፀ 13፥17፤ ዘኍ 14፥3-4 ይመ።

*29፥1* የ5፥2-3 ማብ ይመ። *ኪዳን፤* ሙሴ ከዚህ በፊት እንዳደረገው ሁሉ፣ በዚህም ቦታ የእስራኤል ሕዝብ ከአምላኩ የተቀበለውን ሕግና ሥርዐት መጠበቅ እንዳለበት ያሳስባል። ምክንያቱም ሕጉን መጠበቅ በረከትን ያስገኛል፤ ሕጉን መተላለፍ ደግሞ መርገምን ያመጣል (ዘዳ 28 ይመ)።

29፥2 *ዐይኖቻችሁ አይተዋል፤* ይህን የተባሉት፣ እስራኤላውያን በቃዴስ በርኔ የተስፋዪቱን ምድር እንዲሰልሉ ከተላኩት መካከል አብዛኞቹ ሰላዮች ያመጡትን ቃል በመስማት ወደ ከነዓን ለመግባት እምቢ ባሉ ጊዜ፣ ዕድሜአቸው ከ20 ዓመት በታች የሆኑትና ከግብፅ ከመውጣታቸው በፊት የግብፅን ሕይወት ያዩት ብቻ ናቸው (ዘኍ 14፥29)። ሙሴ ግን ይህንን ያለው የግብፅን ሕይወት ሕዝቡ ሁሉ እንዳየ አድርጎ ነው (የ 5፥3 ማብ ይመ)።

*29፥4፤* ሕዝቡ እግዚአብሔር ያደረገላቸውን በጎ ነገር ሁሉ ማየት ተስኖት ነበር (ከመዝ 106፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህ ቃል በሮሜ 11፥8 ላይ ልባቸውን ያደነደኑትን እስራኤላውያንን አስመልክቶ ተጠ

መጡ፤ ሆኖም ድል አደረግናቸው:: [8]ምድራቸውንም ወስደን፤ ለሮቤላውያን፣ ለጋዳውያንና ለምናሴ ነገድ እኩሌታ ርስት አድርገን ሰጠን::

[9]እንግዲህ የምታደርጉት ሁሉ እንዲከናወንላችሁ፣ የዚህን ኪዳን ቃሎች በጥንቃቄ ተከተሉ:: [10]እናንተ ሁላችሁ መሪዎቻችሁና አለቆቻችሁ፣ ሽማግሌዎቻችሁና ሹሞቻችሁ እንዲሁም ሌሎች የእስራኤል ሰዎች ሁሉ ዛሬ በአምላካችሁ በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ቆማችኋል፤ [11]ልጆቻችሁና ሚስቶቻችሁ እንጨትህን እየፈለጡ፣ ውሃህንም እየቀዱ በሰፈርህ የሚኖሩ መጻተኞችም አብረውህ ቆመዋል:: [12]እዚህ የቆምኸው እግዚአብሔር (ያህዌ) ዛሬ ከአንተ ጋር ወደሚያደርገውና በመሐላ ወደሚያጸናው ኪዳን ከአምላክህ ከእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ጋር ትገባ ዘንድ፣ [13]ለአንተ በሰጠው ተስፋና ለአባቶችህ ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ በማለላቸው መሠረት እርሱ ስምባክህ (ኤሎሂም) ይሆን ዘንድ፣ አንተም ሕዝቡ መሆንህን፣ በዛሬው ዕለት ለማረጋገጥ ነው:: [14]እኔም ይህን የመሐላ ኪዳን የማደርገው ከእናንተ ጋር ብቻ አይደለም፤ [15]አብራችሁን በአምላካችን በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት እዚህ ከቆማችሁት ጋር ብቻ ሳይሆን፣ ዛሬ እዚህ ከሌሉትም ጋር ነው::

[16]በግብፅ ምድር እንዴት እንደ ኖርንና ወደ ዚህ ስንመጣም በየአገሮቹ ውስጥ እንዴት እንዳለፍን ራሳችሁ ታውቃላችሁ:: [17]በመካከላቸውም አስጸያፊ ምስሎቻቸውንና የዕንጨትና የድንጋይ፣ የብርና የወርቅ ጣዖቶቻቸውን አይታችኋል:: [18]የእነዚህን ሕዝቦች አማልክት ለማምለክ ልቡን ከአምላካችን ከእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የሚመልስ ወንድም ሆነ ሴት ጐሣም ሆነ ነገድ ዛሬ ከመካከላችሁ አለመገኘቱን አረጋግጡ፤ ከመካከልህ እንዲህ ያለውን መራራ መርዝ የሚያወጣ ሥር እንዳይኖር ተጠንቀቁ::

[19]እንዲህ ያለው ሰው የዚህን መሐላ ቃል በሚሰማበት ጊዜ፣ በልቡ ራሱን በመባረክ፣ "እንደ ልቤ ሐሳብ ብኖርም እንኳ ሰላም አለኝ" ብሎ ያስባል:: ይህም በለምለሙም ሆነ በደረቁ መሬት ላይ ጥፋትን ያመጣል[u]:: [20]እግዚአብሔር (ያህዌ) ለዚያ ሰው ፈጽሞ ይቅርታ አያደርግለትም፤ ቍጣውና ቅናቱ በእርሱ ላይ ይነድበታል:: በዚህ መጽሐፍ የተጻፈው ርግማን ሁሉ ይወርድበታል፤ እግዚአብሔርም (ያህዌ) ስሙን ከሰማይ በታች ይደመስሰዋል:: [21]በዚህ የሕግ መጽሐፍ በተጻፈው የኪዳኑ ርግማን መሠረት፣ እግዚአብሔር (ያህዌ) እርሱን ከእስራኤል ነገዶች ሁሉ ለጥፋት ይለየዋል::

[22]የሚቀጥለው ትውልድ ከእናንተ በኋላ የሚተኩት ልጆቻችሁና ከሩቅ አገር የሚመጡ እንግዶች በምድሪቱ የደረሰውን ታላቅ መቅሠፍትና እግዚአብሔር (ያህዌ) ያመጣባቸውን በሽታዎች ያያሉ:: [23]ምድሪቱ በሙሉ የተቃጠለ ጨውና ዲን ዐመድ ትሆናለች:: አንዳች ነገር አይተከልባትም፤ ምንም ነገር አያቈጠቍጥባትም፤ የሚያድግ ተክል አይገኝባትም:: የሚደርስባት ውድመት እግዚአብሔር (ያህዌ) በታላቅ ቍጣ እንደ ገለባበጣቸው እንደ ሰዶምና ገሞራ፣ እንደ አዳማና ሲባዮ ጥፋት ይሆናል:: [24]አሕዛብም ሁሉ፣ "እግዚአብሔር (ያህዌ) በዚች ምድር ላይ ይህን ለምን አደረገባት? ይህ አስፈሪና የሚነድ ቍጣስ ለምን መጣባት?" ብለው ይጠይቃሉ::

[25]መልሱም፣ "የአባቶቻቸው ስምባክ (ኤሎሂም) ከግብፅ ምድር ባወጣቸው ጊዜ፣ ከእነርሱ ጋር የገባውን ኪዳን ሕዝቡ ስለ ተዉ ነው:: [26]ወጥተውም የማያውቋቸውን፣ እርሱም ያላዘዛቸውን ሌሎችን አማልክት አመለኩ፤ ሰገዱላቸውም:: [27]ስለዚህ በዚህ መጽሐፍ የተጻፈውን ርግማን ሁሉ እስኪያመጣባት ድረስ፣ የእግዚአብሔር (ያህዌ) ቍጣ በዚህች ምድር ላይ ነደደ:: [28]በአስፈሪ ቍጣና በታላቅ መዓት እግዚአብሔር (ያህዌ) ከምድራቸው ነቀላቸው፤ አሁን እንደ ሆነውም ወደ ሌላ ምድር ጣላቸው" የሚል ይሆናል::

[29]ምስጢር የሆነው ለአምላካችን ለእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ነው፤ የተገለጠው ግን የዚህን ሕግ ቃል ሁሉ እንከተል ዘንድ ለዘላለም የኛና የልጆቻችን ነው::

## ወደ እግዚአብሔር በመመለስ የሚገኝ በረከት

**30** በፊትህ ያስቀመጥሁት ይህ በረከትና መርገም ሁሉ በአንተ ላይ ሲመጣና አምላክህ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በትኖህ በምትኖርበት አሕዛብ መካከል ሆነህ ወደ ልብህ ተመልሰህ ነገሮቹን በምታስተውልበት ጊዜ፣ [2]እንዲሁም ዛሬ እኔ በማዝህ ሁሉ መሠረት አንተና ልጆችህ ወደ አምላካችሁ ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ተመልሳችሁ በፍጹም ልባችሁና በፍጹም ነፍሳችሁ እርሱን ስትታዘዙ፣

ዘዳ2፥26-3፥11
29፥8 ዘኍ32፥33፤ ዘዳ3፥12-13፤ መዝ78፥55፤135፥12፤ 136፥22
29፥9 ዘፀ19፥5፤ ዘዳ4፥6፤ኢያ1፥7፡8፤ 2ዜና31፥21፤ መዝ25፥10፤103፥18
29፥11 ኢያ9፥21፡ 23፡27፤1ዜና20፥3
29፥13 ዘፍ6፥18፤ 17፥7፤ዘፀ19፥6
29፥14 ዘፀ19፥5፤ ኢሳ59፥21፤ ኤር31፥31፤32፥40፤ 50፥5፤ሕዝ16፥62፤ 37፥26፤ዕብ8፥7-8
29፥15 ዘፍ6፥18፤ ሐሥ2፥39
29፥17 ዘፀ20፥23፤ ዘዳ4፥28
29፥18 ዘዳ11፥16፤ 13፥6፤ዕብ12፥15
29፥19 መዝ36፥2፤ 72፥17፤ኢሳ65፥16
29፥20 ዘፀ23፥21፤ 34፥14፤2ነገ13፥23፤ 14፥27፤መዝ74፥1፤ 79፥5፤80፥4፤ ሕዝ23፥25፤36፥5፤ ሶፎ1፥18፤ራእ3፥5
29፥21 ዘዳ28፥61፤ 32፥23፤ሕዝ7፥26
29፥22 ኤር19፥8፤ 49፥17፤50፥13
29፥23 ዘፍ13፥10፤ 14፥8፤19፥24፡25፤ ኢሳ1፥7፤6፥11፤9፥18፤ 64፥10፤ኤር12፥11፤ 44፥2፡6፤ሕዝ47፥11፤ ሚክ5፥11፤ሶፎ2፥9 ማቴ10፥15፤ ሮሜ9፥29
29፥24 1ነገ9፥8፤ 2ዜና36፥19፤ ኤር16፥10፤ 22፥8-9፤52፥13
29፥25 2ነገ17፥23፤ 2ዜና36፥21
29፥27 ዘዳ28፥15
29፥28 2ዜና7፥20፤ 1ነገ14፥15፤መዝ7፥1 1፤9፥6፤52፥5፤ምሳ2፥ 22፤ኤር12፥14፤31፥2 8፥42፤10፤ሕዝ19፥12
29፥29 ሐሥ1፥7፤ 17፥11፤ዮሐ5፥39፤ 2ጢሞ3፥16
30፥1 ዘሌ26፥40-45፤ ዘዳ4፥32፤11፥26፤ 29፥28
30፥2 ዘዳ4፥29፡30፤ መዝ119፥2

[u]19 ወይም፣ *ለመርካት ስካርን ይጨምራል::*
[a]3 ወይም፣ *ከግዞት ይመልስሃል::*

ቅሰአል::

29፥8 *ርስት አድርገን ሰጠን፤* 3፥12-17 ይመ::

*29፥9-15፤* ሕዝቡ የገባውን ኪዳን እንደሚጠብቅ በድጋሚ ያረጋገጠ መሆኑን የሚያሳይ ግልጽና አጭር ማጠቃለያ ነው::

29፥18 *መራራ መርዝ የሚያወጣ ሥር፤* እግዚአብሔርን በመተው ባዕድ አማልክትን የማምለክ መርዝ ነው::

29፥20 *እግዚአብሔር ለዚያ ሰው ፈጽሞ ይቅርታ አያደርግለትም፤* በ2ጴጥ 3፥9 ላይ ("ማንም እንዳይጠፋ") ያለውን ሐሳብ እንደሚቃረን ተደርጎ መታየት የለበትም:: ራሱ ጴጥሮስ እንደሚለው፣ "የዋጃቸውን ጌታ" የሚክዱ "በራሳቸው ላይ ድንገተኛ ጥፋት" ያመጣሉ (2ጴጥ 2፥1):: *በዚህ መጽሐፍ፤* የ31፥24 ማብ ይመ:: *ስሙን ከሰማይ በታች ይደመስሰዋል፤* 9፥14፤ ዘፀ 32፥32-33፤ ራእ 3፥5 ይመ::

29፥21 *የሕግ መጽሐፍ፤* የ31፥24 ማብ ይመ::

29፥23 *እንደ ሰዶምና ... ጥፋት፤* ዘፍ 19፥24-25 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 10፥19፤ 13፥10 ማብ ይመ::

29፥27 *በዚህ መጽሐፍ፤* የ31፥24 ማብ ይመ::

29፥28 *አሁን እንደ ሆነውም፤* እንዲህ ማለት የሚቻለው እስራኤል በተማረከችበት ጊዜ ነበር (ቍ 25 ይመ)::

29፥29 *ምስጢር የሆነው፤* ከበረከቱና ከርግማኑ አንጻር፣ ወደ ፊት ስለሚገለጠው የእስራኤል ዕጣ ፈንታ ማለት ነው፤ ሆኖም አባባሉ ከዚህ በላይ ሰፋ ያለ ትርጒም ሊኖረው ይችላል:: *የተገለጠው፤* ከሁሉ በፊት፣ "የዚህን ሕግ ቃላት" ማለት ነው::

30፥2፡6፡10 *በፍጹም ልባችሁና በፍጹም ነፍሳችሁ፤* የ4፥29

[3]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ምርኮህን ይመልስልሃል[^]፤ ይራራልሃልም፤ አንተን ከበተነበት አሕዛብ መካከል እንደ ገና ይሰበስብሃል። [4]ከሰማይ በታች እጅግ ሩቅ ወደ ሆነ ምድር ብትጋዝ እንኳ፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ከዚያ ይሰበስብሃል፤ መልሶም ያመጣሃል። [5]የአባቶችህ ወደ ሆነችው ምድር ያመጣሃል፤ አንተም ትወርሳታለህ። ከአባቶችህ ይበልጥ ያበለጽግሃል፤ ያበዛሃልም። [6]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) በፍጹም ልብህና በፍጹም ነፍስህ እንድትወደው፣ በሕይወትም እንድትኖር፣ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የአንተንና የዘርህን ልብ ይገርዛል። [7]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ይህን ርግማን ሁሉ በሚጠሉህና በሚያሳድዱህ ጠላቶችህ ላይ ያደርገዋል። [8]አንተም ተመልሰህ *ለእግዚአብሔር* (ያህዌ) ትታዘዛለህ፤ ዛሬ እኔ የማዝህን ትእዛዝ ሁሉ ትጠብቃለህ። [9]ከዚያም *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) በእጅህ ሥራ ሁሉና በወገብህ ፍሬ፣ በእንስሳትህ ግልገሎችና በምድርህ ሰብል እጅግ ያበለጽግሃል። በአባቶችህ ደስ እንደ ተሰኘ ሁሉ፣ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) አንተንም በማበልጸግ ደስ ይለዋልና። [10]ይህም የሚሆነው፣ *አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) ከታዘዝህና በዚህ የሕግ መጽሐፍ የተጻፉትን ትእዛዙንና ሥርዐቱን በመጠበቅ፣ በፍጹም ልብህና በፍጹም ነፍስህ ወደ *አምላክህ* ወደ እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ስትመለስ ነው።

## ሕይወትን ወይም ሞትን ስለ መምረጥ

[11]በዛሬው ዕለት የምሰጥህ ትእዛዝ ይህን ያህል አስቸጋሪ ወይም ከአንተ የራቀች አይደለችም። [12]"እንድንፈጽማት አምጥቶ ይነግረን ዘንድ፣ ማን ወደ ሰማይ ይወጣል?" እንዳትል፣ በላይ በሰማይ አይደለችም። [13]ደግሞም፣ "እንድናደርጋት አምጥቶ ይነግረን ዘንድ፣ ማን ባሕሩን ይሻገራል?" እንዳትልም፣ ከባሕር ማዶ አይደለችም። [14]ነገር ግን ቃሉ ለአንተ በጣም ቅርብ ነው፤ ታደርገውም ዘንድ በአፍህና በልብህ ውስጥ ነው።

[15]እነሆ፤ ዛሬ ሕይወትንና በረከትን፣ ሞትንና ጥፋትን በፊትህ አኑሬአለሁ። [16]*አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትወድ፣ በመንገዱም እንድትሄድና ትእዛዙን፣ ሥርዐቱንና ሕጉን እንድትጠብቅ አዝሃለሁ፤ ከዚያም በሕይወት ትኖራለህ፤ ትበዛለህም፤ *አምላክህም* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ትወርሳት ዘንድ በምትገባበት ምድር ይባርክሃል።

[17]ልቡ ግን ልብህ ወደ ኋላ ቢመለስና ባትታዘዝ፣ ለሌሎች አማልክት ለመስገድ ብትታለልና ብታመልካቸው፣ [18]በርግጥ እንደምትጠፋ እኔ በዛሬው ዕለት እነግራችኋለሁ፤ ዮርዳኖስን ተሻግረህ ትወርሳት ዘንድ በምትገባባት ምድር ብዙ አትኖሩባትም።

[19]ሕይወትንና ሞትን፣ በረከትንና ርግማንን በፊትህ እንዳስቀመጥሁ ዛሬ ሰማይንና ምድርን ምስክር አድርጌ እጠራብሃለሁ። እንግዲህ አንተና ልጆችህ በሕይወት እንድትኖሩ ሕይወትን ምረጥ፤ [20]ይኸውም *አምላክህን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) እንድትወድ፣ ቃሉን እንድታደምጥና ከእርሱ ጋር እንድትጣበቅ ነው። ምክንያቱም *እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሕይወትህ ነው፣ ለአባቶችህ፣ ለአብርሃም፣ ለይስሐቅና ለያዕቆብ ሊሰጣቸው በማለላቸው ምድር ረጅም ዕድሜ ይሰጥሃል።

## ኢያሱ በሙሴ እግር መተካቱ

**31** [1]ከዚያም ሙሴ ወጥቶ እነዚህን ቃሎች ለእስራኤል ሁሉ ተናገረ፤ [2]"እነሆ፤ መቶ ሃያ ዓመት ሆኖኛል፤ ከእንግዲህ ልወጣና ልገባ አልችልም፤ *እግዚአብሔርም* (ያህዌ) 'ዮርዳኖስን አትሻገርም' ብሎኛል፤ [3]*አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ራሱ በፊትህ ቀድሞ ይሄዳል፤ እነዚህንም አሕዛብ ከፊትህ ያጠፋቸዋል፤ አንተም ምድራቸውን ትወርሳለህ፤ *እግዚአብሔር* (ያህዌ) እንደ ተናገረው፣ ኢያሱም አንተን ቀድሞ ይሻገራል። [4]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) የአሞራውያንን ነገሥታት ሴዎንንና ዐግን ከነምድራቸው እንዳጠፋቸው እነዚህንም ያጠፋቸዋል። [5]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) እነርሱን በፊታችሁ አሳልፎ ይሰጣችኋል፤ እናንተም ያዘዝኋችሁን ሁሉ በእነርሱ ላይ ታደርጋላችሁ። [6]ብርቱና ደፋር ሁኑ፤ አትፍሯቸው ወይም

30፥3 ዘፍ11፥4፤ 48፥21፤ዘዳ4፥27፤ 13፥17፤መዝ14፥7፤ 53፥6፤85፥1፤126፥4፤ ኢሳ11፥11፤ኤር12፥15፤ 16፥15፤24፥6፤29፥14፤ 30፥18፤33፥11፤48፥47፤49፥6፤ሕዝ16፥53፤ ኢዩ3፥1
30፥4 ነህ1፥8-9፤ መዝ19፥6፤ ኢሳ11፥12፤17፥6፤ 24፥13፤27፥12፤40፥11፤ 41፥5፤42፥10፤43፥6፤ 48፥20፤49፥5፤56፥8፤ 62፥11፤ኤር10፥50፥2፤ 29፥31፥8፤ሕዝ20፥34፤41፤34፥13
30፥5 ዘዳ7፥13፤ ኤር29፥14
30፥6 ዘዳ6፥5፡24፤ 10፥16
30፥7 ዘፍ12፥3፤ ዘዳ7፥15
30፥9 ዘዳ28፥63፤ ኤር1፥10፥24፥6፤ 31፥28፤34፥41፤ 42፥10፤45፥4
30፥10 ዘዳ5፥29፤ 28፥61
30፥11 መዝ19፥8፤ ኢሳ45፥19፡23፤63፥1
30፥12 ምሳ30፥4፤ ሮሜ10፥6
30፥13 ኢዮ28፥14፤ ሮሜ10፥7
30፥14 ዘዳ6፥6፤ ሮሜ10፥8
30፥15 ዘፍ2፥17፤ ዘዳ11፥26፤28፥11፤ ኢዮ36፥10፤ መዝ25፥13፤106፥5፤ ምሳ3፥1-2፤10፥16፤ 11፥19፤12፥28፤ኤር21፥8
30፥16 ቍ19፤ ዘዳ4፥1፤6፥5፤32፥47፤ ነህ9፥29
30፥18 ዘዳ8፥19
30፥19 ዘዳ4፥26፤ 11፥26
30፥20 ዘፍ12፥7፤ ዘዳ4፥1፤6፥5፤8፥3፤ 32፥47፤ መዝ27፥1፤37፥3፤ ምሳ3፥22፤ዮሐ5፥26፤ ሐሥ17፥28
31፥2 ዘፀ7፥7፤ ዘኍ27፥17፤ ዘዳ3፥23፡26፤1ነገ3፥7
31፥3 ዘኍ27፥18፤ ዘዳ3፥28፤7፥1፤9፥3
31፥4 ዘኍ21፥33
31፥5 ዘዳ2፥33
31፥6 ቍ7፥23፤ ዘፍ28፥15፤ዘዳ1፥29፤4፥31፤20፥4፤ኢሱ1፥6፡ 9፡18፤10፥25፤

ማብ ይመ።

30፥3 *ምርኮህን ይመልስልሃል፤* "ከምርኮ አገር ይመልስሃል" ማለት ሊሆን ይችላል።

30፥6 *ልብ ይገርዛል፤* የዘፍ 17፥10 ማብ ይመ።

30፥7 *ርግማን ሁሉ በሚጠሉህ፤* እዚህ ላይ በዘፍ 12፥3 የተጠቀሰው ቃል ተፈጽሞአል።

30፥9 *በአባቶችህ፤* ርእሳን አበው ማለት ነው (ቍ 20 ይመ)።

30፥10 *የሕግ መጽሐፍ፤* የ31፥24 ማብ ይመ።

30፥12፡14 *በላይ በሰማይ አይደለችም ... ለአንተ በጣም ቅርብ ነው፤* የኪዳኑን ሕግ ለማስተዋል፣ ለማመንና ለመታዘዝ ከእነርሱ ዐቅም በላይ እንዳልሆነ ሙሴ ይገልጽላቸዋል። ጳውሎስ ይህንን ክፍል፣ "የእምነት ቃል" ቅርብ መሆኑን ለመግለጽ ተጠቅሞበታል (ሮሜ 10፥6-10)።

30፥19 *ሰማይና ምድርን ምስክር አድርጌ እጠራብሃለሁ፤* ከብሉይ ኪዳን ውጭ የሚገኙ የጥንት ቃል ኪዳኖች ለተገባው ኪዳን፣ "ምስክር" የሚሆኑ የአማልክትን ስም ዝርዝር ይዘዋል። በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ የሚገኘው ቃል ኪዳን ግን፣ "ምስክር" አድርጎ የጠራው ሰማይንና ምድርን ነው (31፥28፤ 32፥1 ይመ፤ እንዲሁም የመዝ 50፥1፤ የኢሳ 1፥2 ማብ ይመ)።

30፥20 *ከእርሱ ጋር እንድትጣበቅ፤* የ10፥20 ማብ ይመ። *እግዚአብሔር ሕይወትህ ነው፤* እግዚአብሔርን ሲመርጡ ሕይወትን መርጠዋል (ቍ 19)። በ32፥46-47 ላይ፣ "የዚህ ሕግ ቃላት ሁሉ" የተባለው ሕይወታቸው እንደ ሆነ ተመልክቶአል። ሕጉ፣ እግዚአብሔርና ሕይወት የማይነጣጠሉ ናቸው። በዚህ ዐውድ፣ "ሕይወት" የሚለው ቃል የሚያመለክተው እግዚአብሔር ሲፈጥረው ይሆን ዘንድ ባሰበው መሠረት ሕይወትን ሙሉና ፍሬያማ የሚያደርገውን ነገር ነው።

31፥2 *ከእንግዲህ ልወጣና ልገባ አልችልም፤* የአካሉን ወይም የሰውነቱን መድከም ብቻ ላያመለክት ይችላል (34፥7 ይመ)። ከኀጢአቱ የተነሣም ሙሴ የእስራኤልን ሕዝብ እንዲመራ እግዚአብሔር አልፈቀደለትም ነበር (1፥37፤ 3፥23-27፤ 4፥21-22፤ 32፥48-52፤ ዘኍ 20፥2-13 ይመ)።

31፥4 *ሴዎንንና ዐግን ከነምድራቸው እንዳጠፋቸው፤* 2፥26-3፥11 ይመ።

31፥6 *ብርቱና ደፋር ሁኑ፤* እግዚአብሔር በአገልጋዮቹ አማካይነት ለእስራኤል ሕዝብ (ኢሱ 10፥25)፣ ለኢያሱ (ቍ 7፡23፤ ኢሱ

አትደንግጡላቸው፡፡ *አምላክህ* እግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ካንተ ጋር ይሄዳልና፤ አይተውህም፤ አይጥልህምም፡፡"

[7]ከዚያም ሙሴ ኢያሱን ጠርቶ በእስራኤል ሁሉ ፊት እንዲህ አለው፤ "*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ለአባቶቻቸው ሊሰጥ ወደ ማለላቸው ምድር ከዚህ ሕዝብ ጋር አብረህ ስለምትገባ፣ ምድሪቱን ርስታቸው አድርገህ ስለምታከፋፍል በርታ፤ ደፋርም ሁን፡፡ [8]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ራሱ በፊትህ ይሄዳል፤ ከአንተም ጋር ይሆናል፤ ፈጽሞ አይለይህም፤ አይተውህምም፤ አትፍራ፤ ተስፋም አትቍረጥ፡፡"

## ሕጉን ለማንበብ ትእዛዝ ስለ መሰጠቱ

[9]ሙሴም ይህን ሕግ ጽፎ፣ *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) የኪዳን ታቦት ለሚሸከሙ ለሌዊ ልጆች፣ ለካህናቱና ለእስራኤል አለቆች ሁሉ ሰጠ፡፡ [10]ከዚያም በኋላ ሙሴ እንዲህ ሲል አዘዛቸው፤ "ዕዳ በሚተውበት፣ የዳስ በዓልም በሚከበርበት፣ በየሰባቱ ዓመት መጨረሻ፣ [11]እስራኤል ሁሉ እርሱ በሚመርጠው ስፍራ *በአምላክህ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) ፊት ሲታይ ይህን ሕግ በእነርሱ ፊት በጆሮአቸው ታነበዋለህ፡፡ [12]ይሰሙና *አምላካችሁን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) መፍራት ይማሩ ዘንድ፣ የዚህን ሕግ ቃል ሁሉ በጥንቃቄ እንዲከተሉ ሕዝቡን ይኸውም ወንዶችን፣ ሴቶችን፣ ልጆችንና በከተሞችህ የሚኖረውንም መጻተኛ ሰብስብ፡፡ [13]ዮርዳኖስን ተሻግረህ በምትወርሷት ምድር በምትኖሩበት ዘመን ሁሉ ይህን ሕግ የማያውቁት ልጆቻቸውም መስማትና *አምላካችሁን* እግዚአብሔርን (ያህዌ ኤሎሂም) መፍራት ሊማሩ ይገባቸዋል፡፡

## የእስራኤል አለመታዘዝ አስቀድሞ ስለ መነገሩ

[14]*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ሙሴን፣ "እነሆ የምትሞትበት ቀን ቀርቦአል፤ ትእዛዝ እንድሰጠው ኢያሱን ጥራውና ወደ መገናኛው ድንኳን ቅረቡ፡፡" ሙሴና ኢያሱም ሄዱ፤ ወደ መገናኛው ድንኳንም ቀረቡ፡፡

[15]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) በድንኳኑ ላይ በደመና ዐምድ ተገለጠ፤ የደመናውም ዐምድ ከድንኳኑ ደጃፍ ላይ ቆመ፡፡ [16]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፡- "እነሆ፣ ከአባቶችህ ጋር ልታርፍ ነው፤ ይህም ሕዝብ በሚገባበት ምድር በሚገኙ ባዕዳን አማልክት ወዲያውኑ ያመነዝራል፡፡ እኔን ይተወኛል፤ ከእነርሱም ጋር የገባሁትን ኪዳን ያፈርሳሉ፡፡ [17]በዚያች ቀን እቈጣቸዋለሁ፤ እተዋቸዋለሁም፤ ፊቴን ከእነርሱ እሰውራለሁ፤ እነርሱም ይጠፋሉ፡፡ ብዙ ጥፋትና የከፋ ችግር ይደርስባቸዋል፤ በዚያችም ቀን፣ 'ይህ ጥፋት የደረሰብን፣ አምላካችን (ኤሎሂም) ከእኛ ጋር ባለመሆኑ አይደለምን?' ይላሉ፡፡ [18]ወደ ባዕዳን አማልክት በማዘር ከፈጸሙት ክፋታቸው የተነሣ በዚያች ቀን ፊቴን ከእነርሱ ፈጽሞ እሰውራለሁ፡፡

[19]"እንግዲህ ይህን መዝሙር ለራሳችሁ ጻፉ፤ ለእስራኤል ልጆችም አስተምሩ፤ ስለ እኔ ምስክር ይሆንባቸው ዘንድ እንዲዘምሩ አድርጉ፡፡ [20]ወተትና ማር ወደምታፈሰውና ለአባቶቻቸው በመሐላ ቃል ወደ ገባሁላቸው ምድር ባመጣኋቸው ጊዜ ከበሉና ከጠገቡ፣ ከበለጸጉም በኋላ እኔን ንቀው ኪዳኔንም አፍርሰው ወደ ባዕዳን አማልክት ይዞራሉ፤ እነርሱንም ያመልካሉ፡፡ [21]ብዙ ጥፋትና የከፋ ችግር በደረሰባቸው ጊዜ ይህ መዝሙር ምስክር ይሆንባቸዋል፡፡ በዘራቸው የሚረሳ አይደለምና፡፡ ወደ ማልሁላቸው ምድር ሳላስገባቸው በፊት ምን ለማድረግ እንደሚያስቡ እንኳን አስቀድሜ ዐውቃለሁ፡፡" [22]ስለዚህም ሙሴ ይህን መዝሙር በዚያች ቀን ጻፈ፤ ለእስራኤላውያንም አስተማራቸው፡፡

[23]*እግዚአብሔርም* (ያህዌ) ለነዌ ልጅ ለኢያሱ፣ "በርታ፤ ደፋር ሁን፤ የእስራኤልን ልጆች በመሐላ ቃል ወደ ገባሁላቸው ምድር ታስገባቸዋለህና፤ እኔም ከአንተ ጋር እሆናለሁ" በማለት ትእዛዝ ሰጠው፡፡

[24]ሙሴ ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ የዚህን ሕግ ቃል በመጽሐፍ ጽፎ እንዳበቃ፣ [25]*የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) የኪዳን ታቦት የሚሸከሙ ሌዋውያንን እንዲህ ሲል አዘዛቸው፤ [26]"በእናንተ ላይ ምስክር ሆኖ በዚያ ይኖር ዘንድ *በአምላካችሁ* በእግዚአብሔር (ያህዌ ኤሎሂም) የኪዳን ታቦት አጠገብ አስቀምጡት፤ ይህም በእናንተ ላይ ምስክር ሆኖ በዚያ ይኖራል፤ [27]የቱን ያህል ዐመፀኞችና ዐንገተ ደንዳኖች እንደ ሆናችሁ ዐውቃለሁና፡፡ እኔ በሕይወት ከእናንተ ጋር እያለሁ እንደዚህ ካመፃችሁ፣ ከሞትሁ በኋላማ የቱን ያህል

31፥6፤ 1ሳሙ 12፥22፤ 1ነገ 6፥13፤ 1ዜና 22፥13፤ 28፥20፤ 2ዜና 32፥7፤ መዝ 56፥9፤ 94፥14፤ 118፥6፤ ኢሳ 41፥17፤ ኤር 1፥8፡17፤ ሕዝ 2፥6፤ ማቴ 28፥20፤ ዕብ 13፥5
31፥7 ቍ 23፤ ዘኍ 27፥23፤ ኢያ 1፥6
31፥8 ዘፍ 28፥15፤ ዘፀ 13፥21፤ ዘዳ 4፥31
31፥9 ቍ 25፤ ዘፀ 17፥14፤ 1ዜና 15፥2
31፥10 ዘፀ 23፥16፤ ዘዳ 15፥1፤ 16፥13
31፥11 ዘዳ 12፥5፤ 16፥16፤ ኢያ 8፥34-35፤ 2ነገ 23፥2፤ ነህ 8፥2
31፥12 ዘዳ 4፥10፤ ሐጌ 1፥12፤ ሚል 1፥6፤ 3፥5፡16
31፥13 ዘዳ 11፥2
31፥14 ዘፍ 25፥8፤ ዘፀ 33፥9-11፤ ዘኍ 27፥13፡19፡23፤ ዘዳ 34፥9፤ ኢያ 1፥1-9
31፥15 ዘፀ 33፥9
31፥16 ዘፍ 15፥15፤ ዘፀ 34፥15፤ ዘዳ 4፥25-28፤ መሳ 2፥12፤ 10፥6፡13፤ 1ነገ 9፥9፤ 18፥18፤ 19፥10፤ ኤር 2፥13፤ 5፥19፤ 19፥4
31፥17 ዘኍ 14፥42፤ ዘዳ 32፥16፡20፤ መሳ 2፥14፡20፤ 6፥13፤ 10፥7፤ 2ነገ 13፥3፤ 22፥13፤ 2ዜና 15፥2፤ 24፥20፤ ዕዝ 8፥22፤ ኢዮ 13፥24፤ መዝ 13፥1፤ 27፥9፤ 30፥7፤ 44፥9፤ 104፥29፤ 106፥29፡40፤ ኢሳ 1፥15፤ 2፥6፤ 45፥15፤ 50፥6፤ 53፥3፤ 54፥8፤ ኤር 4፥20፤ 7፥18፤ 21፥5፤ 33፥5፤ 36፥7፤ ሕዝ 7፥26፤ ሕዝ 39፥29፤ ሆሴ 9፥12፤ ሚክ 3፥4
31፥19 ቍ 22፤ ዘፍ 31፥50
31፥20 ቍ 16፤ ዘፍ 6፥10-12፤ ዘዳ 6፥10-12፤ 8፥19፤ 11፥16-17፤ መዝ 4፥2፤ 16፥4፤ 40፥4፤ ኤር 13፥25፤ ዳን 3፥28፤ አሞ 2፥4
31፥21 ዘዳ 4፥30፤ 1ዜና 28፥9፤ ሆሴ 5፥3፤ ዮሐ 2፥24-25
31፥22 ቍ 19
31፥23 ቍ 7፤ ኢያ 1፥6 31፥24 ዘዳ 17፥18፤ 28፥58፤ 2ነገ 22፥8
31፥25 ቍ 9 31፥26 ቍ 19 31፥27 ዘፀ 23፥21፤ ዘዳ 9፥27

1፥6-7፡9፡18)፣ ለሰሎሞን (1ዜና 22፥13፤ 28፥20) እንዲሁም ለሕዝቅያስ ወታደር አዛዦች (2ዜና 32፥7) የሚሰጠው የማበረታቻ ቃል ነው፡፡ ምንም ያህል ብርቱ ፈተና ቢያጋጥማቸውም፣ እግዚአብሔርን በመታመንና በመታዘዝ በእርሱ መንገድ የሚሄዱ አሸናፊዎች ይሆናሉ፡፡ *አይለይህም፤ አይተውህም፤* ቍ 8፤ ኢያ 1፥5፤ 1ነገ 8፥57 ይመ፡፡ እንዲሁም የዘፍ 28፥15 ማብ ይመ፡፡

31፥9 *ይህን ሕግ ጽፎ ... ለካህናቱ ... ሰጠ፤* በጥንት ዘመን በሕዝቦች መካከል ውል ሲደረግ፣ የውሉ ቅጅ በተዋዋዮቹ የአምልኮ ማእከል በሆኑ ስፍራዎች በአማልክት ፊት ይቀመጥ ነበር፡፡ እስራኤላውያን ግን የኪዳኑን ሕግ ማስቀመጥ ያለባቸው በታቦቱ ላይ ነው (33፥9 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 16፥34፤ 31፥18 ማብ ይመ)፡፡

31፥10 *በየሰባቱ ዓመት፤* 15፥4 እና ማብ፤ ዘፀ 23፥10-11፤ ዘሌ 25፥17 ይመ፡፡ እንዲሁም በገጽ 178 ላይ፣ "የብሉይ ኪዳን በዓላትና ሌሎች የተቀደሱ ቀናት" የሚለውን ይመ፡፡

31፥11 *በሚመርጠው ስፍራ፤* የ12፥5 ማብ ይመ፡፡ *ይህን ሕግ በእነርሱ ፊት በጆሮአቸው ታነበዋለህ፤* የሕጉን ቃል ለእስራኤል ሕዝቦች ማንበብ እንዲሁም ማስተማር የካህናት አንዱ ዋና ተግባር ነው (33፥10፤ ሚል 2፥4-9 ይመ)፡፡

31፥14 *ትእዛዝ እንድሰጠው፤* ቍ 23 ይመ፤ ከዘኍ 27፥18-23 ጋር ያነጻጽሩ፡፡

31፥19 *ይህን መዝሙር ለራሳችሁ ጻፉ፤ ለእስራኤል ልጆችም አስተምሩ፤* ቍ 22፤ 31፥30-32፥43 ይመ፡፡

31፥23 *በርታ፤ ደፋር ሁን፤* የቍ 6 ማብ ይመ፡፡

31፥24 *ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ የዚህን ሕግ ቃል፤* በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ ከመጀመሪያው ምዕራፍ አንሥቶ እስከዚህ ድረስ ያለውን ለማለት ነው (የቍ 9 ማብ ይመ)፡፡

31፥26 *የኪዳን ታቦት አጠገብ አስቀምጡት፤* የቍ 9 ማብ ይመ፡፡

31፥27 *ዐንገተ ደንዳኖች፤* 9፥6፡13፤ 10፥16 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 32፥9 ማብ ይመ፡፡

ሊታምፁ! 28ይህን ቃል ይሰሙ ዘንድ እንድናገር፣ ሰማይንና ምድርን ምስክር አድርጌ እንድጠራባቸው፣ የነገድ አለቆቻችሁን በሙሉና ሹሞቻችሁን ሁሉ በፊቴ ሰብስቡ። 29እኔ ከሞትሁ በኋላ ፈጽማችሁ እንደምትረክሱ፣ ካዘዝኋችሁም መንገድ ዘወር እንደምትሉ ዐውቃለሁና። *በእግዚአብሔር* (ያህዌ) ፊት ክፉ ድርጊት ስለምትፈጽሙ፣ እጆቻችሁ በሠሯቸውም ነገሮች እርሱን ለቍጣ ስለምታነሣሡት፣ በሚመጡት ዘመናት ጥፋት ይደርስባችኋል።"

## የሙሴ መዝሙር

30ሙሴም የዚህን መዝሙር ቃል ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ ድረስ፣ ለተሰበሰበው የእስራኤል ሕዝብ ሁሉ በጆሮአቸው እንዲህ ሲል አሰማ፦

**32** ሰማያት ሆይ፤ አድምጡ፤ እኔም እናገራለሁ፤
ምድር ሆይ፤ አንቺም የአፌን ቃል ስሚ።
2ትምህርቴ እንደ ዝናብ ትውረድ፤
ቃሌም እንደ ጤዛ ይንጠባጠብ፤
በቡቃያ ሣር ላይ እንደ ካፊያ፣
ለጋ ተክልም ላይ እንደ ከባድ ዝናብ ይውረድ።
3እኔ *የእግዚአብሔርን* (ያህዌ) ስም ዐውጃለሁ፤
የአምላካችንን (ኤሎሂም) ታላቅነት አወድሱ!
4እርሱ ዐለት፣ ሥራውም ፍጹም ነው፤
መንገዱም ሁሉ ትክክል ነው፤
የማይሳሳት ታማኝ አምላክ፣
ቀጥተኛና ጻድቅ አምላክም (ኤሎሂም) እርሱ ነው።
5በእርሱ ላይ ክፋት ፈጽመዋል፤
ከነውራቸው የተነሣ ከእንግዲህ ልጆቹ አይደሉም፤
ወልጋዳና ጠማማ ትውልዶች ናቸውሐ።
6አንተ ተላላና ጥበብ የጐደለህ ሕዝብ፣
*ለእግዚአብሔር* (ለያህዌ) የምትመልሰለት በዚህ መንገድ ነውን?
አባትህ ፈጣሪህመ፣
የሠራህና ያበጀህ እርሱ አይደለምን?
7የጥንቱን ዘመን አስታውስ፤
አባትህን ጠይቅ፤ ይነግርሃልም፤
ሽማግሌዎችህንም ጠይቅ፤ ያስረዱሃል።
8ልዑል ለአሕዛብ ርስታቸውን በሰጠ ጊዜ፣
የሰውንም ዘር በለያየ ጊዜ፣
በእስራኤል ልጆችሠ ቍጥር ልክ፣
የአሕዛብን ርስት ድንበር ለየ፤
9*የእግዚአብሔር* (ያህዌ) ድርሻ የገዛ ሕዝቡ፣
ያዕቆብ የተለየ ርስቱ ነውና።
10እርሱን በምድረ በዳ፣
ባዶና ጭው ባለ በረሓ ውስጥ አገኘው፤
ጋሻ ሆነው፤ ተጠነቀቀለትም፤
እንደ ዐይኑ ብሌን ጠበቀው።
11ንስር ጎጆዋን በትና፣
በጫጩቶቿም ላይ እንደምትረብብ፣
እነርሱን ለመያዝ ክንፎቿን እንደምትዘረጋ፣
በክንፎቿም እንደምትሸከማቸው፣
12*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ብቻ መራው፤
ምንም ባዕድ አምላክ አብሮት አልነበረም።
13በምድር ከፍታ ላይ አወጣው፤
የዕርሻንም ፍሬ መገበው፤
ከዐለት ድንጋይ ማር አበላው፤
ከባልጩትም ድንጋይ ዘይት መገበው።
14የላሙንና የበጉን መንጋ ቅቤና ወተት፣
የሰቡትን በጎችና ፍየሎች፣
የባሳንን ምርጥ አውራ በግ፣
መልካም የሆነውንም ስንዴ፣
ማለፊያውንም የወይን ጠጅ፣
15ይሹሩንረ ወፈረ፤ ረገጠ፤
ጠገበ፤ ሰውነቱ ደነደነ፤ ለሰለሰ፤
የፈጠረውንም አምላክ (ኤሎሂም) ተወ፤
መጠጊያ ዐለት የሆነውን አዳኙንም ናቀ።
16በባዕዳን አማልክታቸው አስቀኑት፤
በአስጸያፊ ጣዖቶቻቸውም አስቈጡት።
17አምላክ ላልሆኑ አጋንንት፦
ላላወቋቸው አማልክት፣
ከጊዜ በኋላ ለተነሡ አማልክት፣
አባቶቻችሁ ላልፈሯቸው አማልክት ሠዉ።
18አባት የሆነህን ዐለት ከዳኸው፤
የወለደህን አምላክ (ኤሎሂም) ረሳኸው።
19*እግዚአብሔር* (ያህዌ) ይህን አይቶ ናቃቸው፤
በወንድና በሴት ልጆቹ ተቈጥቶአልና።

31፥28 ዘዳ4፥26፤ 30፥19፤32፥1፤ኢ.የ20፥27፤ኢሳ26፥21
31፥29 ዘዳ4፥16፤1ነገ9፥9፤ 22፥23፤2ነገ22፥16፤ ራእ9፥20
32፥1 ዘዳ4፥26፤ መዝ49፥1፤ኤር2፥12፤ ሚክ1፥2
32፥2 2ሳሙ23፥4፤ መዝ65፥10፤68፥9፤ 72፥6፤107፥20፤ 147፥8፤ኢሳ9፥8፤ 55፥11፤ሚክ5፥7
32፥4 ዘፍ18፥25፤ 49፥24፤ዘዳ4፥35፤ 2ሳሙ22፥31፤ መዝ18፥30፤19፥7፤ 92፥15
32፥5 ቍ20፤ ማቴ17፥17፤ሉቃ9፥41፤ ሐሥ2፥40
32፥6 ቍ15፡28፤ ዘፀ4፥22፤2ሳሙ7፥24፤ መዝ94፥8፤116፥12፤ ኤር5፥21
32፥7 ዘፀ10፥2፤ ዘዳ4፥32፤ኢ.ዮ8፥8፤ 15፥18፤20፥4፤ መዝ44፥1፤74፥2፤ 77፥5፤78፥4፤ ኢሳ46፥9፤
32፥8 ዘፍ11፥8፤ ዘኍ23፥9፤ዘዳ33፥12፡ 28፤መዝ7፥8፤74፥17፤ ኤር23፥6፤ሐሥ8፥1
32፥9 ዘዳ9፥29፤ 1ሳሙ26፥19፤ መዝ16፥5፤73፥26፤ 119፥57፤142፥5፤ ኤር10፥16
32፥10 ዘፀ19፥4፤ ዘዳ1፥19፤8፥15፤ ኢዮ12፥24፤መዝ17፥8፤ 32፥10፤107፥40፤ ምሳ7፥2፤ኤር31፥22፤ ሆሴ13፥5፤ዘካ2፥8
32፥11 ዘፀ19፥4፤ መዝ17፥8፤18፥10-19፤ 61፥4
32፥12 ቍ39፤ ዘዳ4፥35፤መሳ2፥12፤ መዝ18፥31፤81፥9፤ 106፥9፤ኢሳ43፥12፤ 45፥5፤63፥13፤ ኤር31፥32
32፥13 ዘዳ8፥8፤ 33፥24፡29፤ 2ሳሙ22፥34፤ ኢዮ29፥6፤መዝ18፥33፤ ኢሳ33፥16፤58፥14፤ ሕዝ36፥2፤ዕብ3፥19
32፥14 ዘፍ49፥11፤ ዘኍ21፥33፤መዝ65፥9፤ 81፥16፤147፥14
32፥15 ዘፍ49፥24፤ ዘዳ31፥20፡16፤ 33፥5፤ኢሳ1፥4፡ 28፤44፥2፤58፥2፤65፥11፤ኤር5፥28፤ 15፥6፤ሕዝ14፥5፤
32፥16 ዘኍ25፥11፤ዘዳ31፥17፤ 1ነገ14፥9፤1ቆሮ10፥22
32፥17 ዘፀ32፥8፤22፥20፤ዘዳ28፥64፤ መሳ5፥8፤1ቆሮ10፥20
32፥18 መሳ3፥7፤1ሳሙ12፥9፤መዝ44፥17፡20፤ 106፥21፤ኤር2፥32፤ ሕዝ23፥35፤ ሆሴ8፥14፤13፥6 32፥19 ዘሌ26፥30፤ መዝ78፥59፤ አሞ6፥8

ሐ5 ወይም *የተጣመሙት እነርሱ እንጂ የእርሱ ልጆች አይደሉም*።
መ6 ወይም *ያወጣህ አባትህ*።
ሠ8 የማሶሬቱ ቅጅ፣ የሙት ባሕር ጥቅል እንዲሁም የሰብዓ ሊቃናት ትርጉም፣ *የእግዚአብሔር ልጆች* ይላሉ።
ረ15 ይሹሩን ማለት *ቅን* ወይም *ትክክለኛ* ማለት ሲሆን፣ ይኸውም እስራኤልን የሚያሳይ ነው።

31፥28 *ሰማይንና ምድርን ምስክር አድርጌ፤* የ30፥19 ማብ ይመ።

31፥29 *እጆቻችሁ በሠሯቸውም ነገሮች፤* የጣዖት ምስሎችን ለማለት ነው (4፥28፤ 27፥15 እና ማብ ይመ)።

*31፥30-32፥43፤* ይህ ክፍል የሙሴ መዝሙር በመባል ይታወቃል (የዘፀ 15፥1-18፤ የራእ 15፥3 ማብ ይመ)።

32፥1 *ሰማያት ሆይ፤ አድምጡ፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆኑ የመግቢያ ቃሎችን በኢሳ 1፥2 እና ማብ፤ 34፥1፤ ሚክ 1፥2፤ 6፥1-2 ላይ ይመ።

32፥4 *እርሱ ዐለት ... ነው፤* የሙሴ መዝሙር ዋና ሐሳብ ነው (ቍ 15፡18፡30-31 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 49፥24 ማብ ይመ)።

32፥5 *ወልጋዳና ጠማማ ትውልዶች፤* ፊል 2፥15 ይመ።

32፥6 *አባትህ፤* ኢሳ 63፥16፤ 64፥8 ይመ።

32፥7 *የጥንቱን ዘመን አስታውስ፤* የ4፥10 ማብ ይመ።

32፥8 *ልዑል፤* በዘዳግም መጽሐፍ ውስጥ እግዚአብሔር በዚህ ስም የተጠራው እዚህ ቦታ ብቻ ነው (የዘፍ14፥19 ማብ ይመ)። እግዚአብሔር በፍጥረት ሁሉ ላይ ጌታና ገዥ መሆኑን የሚያስገነዝብ ስም ነው። *የሕዝብን ርስት ድንበር ለየ፤* ዘፍ 10 ይመ። *በእስራኤል ልጆች ቍጥር ልክ፤* የሕዝቡ ቍጥር ምንም ያህል ሊጨምር ቢችል፣ እግዚአብሔር ለሁሉም የሚበቃ ርስት አድርጎ ከነዓንን እንደሚሰጣቸው የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (የዘፍ 10፥2 ማብ ይመ)።

32፥10 *እንደ ዐይኑ ብሌን፤* ይህም የሚያመለክተው በቀላሉ ሊጐዳ የሚችለውን፣ ለማየት በጣም አስፈላጊ የሆነውንና የተከፈለው ዋጋ ተከፍሎ ልዩ ጥንቃቄ ሊደረግለት የሚገባውን የዐይንን ብሌን ነው።

32፥11 *በላያቸውም እንደምትረብብ፤* የዘፍ 1፥2 ማብ ይመ።

32፥13 *ከዐለት ድንጋይ ማር፤* መዝ 81፥16 ይመ። *ከባልጩት ድንጋይ ዘይት፤* ኢዮ 29፥6 ይመ።

32፥14 *ባሳን፤* የሕዝ 39፥18 ማብ ይመ። *ማለፊያውንም የወይን ጠጅ፤* ዘፍ 49፥11 ይመ።

32፥15 *ይሹሩን፤* የስሙ ትርጉም "ቅን የሆነ" ማለት ሲሆን፣

[20]እርሱም፣ "ፊቴን ከእነርሱ እሰውራለሁ፤"
"መጨረሻቸው ምን እንደሚሆንም አያለሁ አለ፤
ጠማማ ትውልድ፣
የማይታመኑም ልጆች ናቸውና።
[21]አምላክ ባልሆነው አስቀኑኝ፤
በከንቱ ጣዖቶቻቸው አስቈጡኝ።
እኔም ሕዝብ ባልሆነው አስቀናቸዋለሁ።
በማያስተውልም ሕዝብ አስቈጣቸዋለሁ።
[22]በቍጣዬ እሳት ተቀጣጥሎአልና፤
እርሱ እስከ ሲኦል ዘልቆ ይነዳል።
ምድርን እስከ ሰብሏ ይበላል፤
የተራሮችንም መሠረት ያቀጣጥላል።
[23]"በመዓት ላይ መዓት አመጣባቸዋለሁ።
ፍላጻዬንም በእነርሱ ላይ እጨርሳለሁ።
[24]የሚያጠፋ ራብ፣
በልቶ የሚጨርስ ቸነፈርና ከባድ መቅ
ሠፍት እሰድባቸዋለሁ፤
የአራዊትን ሹል ጥርስ፣
በምድር የሚሳብ የእባብ መርዝም እሰድ
ባቸዋለሁ።
[25]ሰይፍ መንገድ ላይ ያስቀራቸዋል፤
ቤታቸውም ውስጥ ድንጋጤ ይነግሣል፤
ጕልማሳውና ልጃገረዷ፣
ሕፃኑና ሽማግሌው ይጠፋሉ።
[26]እበትናቸዋለሁ፤
ከሰዎችም መካከል መታሰቢያቸውን አጠ
ፋለሁ አልሁ፤
[27]ነገር ግን ጠላቶቻቸው እንዳይታበዩ፣
'ድል ያደረገችው እጃችን እንጂ፣
እግዚአብሔር (ያህዌ) ይህን ሁሉ አላደረገም
እንዳይሉ፣'"
የጠላትን መነሣሣት ሠጋሁ።
[28]አእምሮ የጐደላቸው፣
ማስተዋልም የሌላቸው ናቸው።
[29]አስተዋዮች ቢሆኑ ኖሮ ይህን በተገነዘቡ፣
መጨረሻቸውም ምን እንደሚሆን ባስተዋሉ
ነበር።
[30]መጠጊያ ዐለታቸው ካልሸጣቸው፣
እግዚአብሔር (ያህዌ) ካልተዋቸው በቀር፣
አንድ ሰው እንዴት ሺሁን ያሳድዳል?
ሁለቱስ እንዴት ዐሥር ሺሁን እንዲሸሹ
ያደርጋሉ?
[31]የእነርሱ መጠጊያ ዐለት እንደ እኛ መጠጊያ
ዐለት አይደለምና፤
ጠላቶቻችንም እንኳ ይህን አይክዱም።
[32]ወይናቸው ከሰዶም ወይን፣
ከገሞራም እርሻ ይመጣል፤
የወይናቸው ፍሬ በመርዝ፣
ዘለላቸውም በምሬት የተሞላ ነው።
[33]ወይናቸው የእባብ መርዝ፣
የመራዥ እባብም መርዝ ነው።
[34]"ይህ በእኔ ዘንድ ተጠብቆ ያለ፣
በመዝገቤስ የታተመ አይደለምን?
[35]በቀል የእኔ ነው፤ እኔ ብድራትን እመልሳለሁ፤
ጊዜው ሲደርስ እግራቸው ይሰናከላል፤
የመጥፊያቸው ቀን ቀርቦአል፤
የሚመጣባቸውም ፍርድ ፈጥኖባቸዋል።"
[36]ኀይላቸው መድከሙን፣
ባሪያም ሆነ ነጻ ሰው አለመቅረቱን በሚያዩበት
ጊዜ፣
እግዚአብሔር (ያህዌ) ለሕዝቡ ይፈርዳል፤
ለአገልጋዮቹም ይራራል።
[37]እንዲህም ይላል፤ "መጠጊያ ዐለት የሆናቸው፣
እነዚያ አማልክታቸው የት አሉ?
[38]የመሥዋዕታቸውን ስብ የበሉ፣
የመጠጥ ቍርባናቸውንም የወይን ጠጅ
የጠጡ አማልክት ወዴት ናቸው?
እስቲ ይነሡና ይርዷችሁ!
እስቲ መጠለያ ይስጧችሁ!
[39]"እኔ ራሴ እርሱ እንደ ሆንሁ እዩ፤
ከእኔም በቀር ሌላ አምላክ የለም፤
እገድላለሁ፤ አድናለሁም፤
አቈስላለሁ፤ እፈውሳለሁም፤
ከእጄም የሚያስጥል ማንም የለም።
[40]እጄን ወደ ሰማይ አነሣለሁ፤
ለዘላለምም ሕያው እንደ ሆንሁ እናገራለሁ፤
[41]የሚያብረቀርቅ ሰይፌን ስዬ፣
እጄ ለፍርድ ስትይዘው፣
ባላጋራዎቼን እበቀላቸዋለሁ፤
የሚጠሉኝንም እንደ ሥራቸው እከፍላቸዋለሁ።
[42]ሰይፌ ሥጋ በሚበላበት ጊዜ፣
ፍላጻቼ በደም እንዲሰክሩ አደርጋለሁ፤
ደሙ የታረዱትና የምርኮኞች፣
የጠላት አለቆችም ራስ ደም ነው።"
[43]አሕዛብ ሆይ፤ ከሕዝቡ ጋር ደስ ይበላችሁ[ሀ][ለ]፤

32፥20 ቍ5፤ ዘጸ9፥23፤31፥17፡29፤ መዝ4፥6፤44፥24 32፥23 ቍ42፤ ዘጸ29፥21፤2ሳሙ22፥15 ኢዮ6፥4፤መዝ7፥13፤ 18፥14፤45፥5፤77፥17፤ 120፥4፤ኢሳ5፥28፤ 49፥2፤ሕዝ5፥16፤ ዕን3+9፡11 32፥24 ቍ33፤ ዘፍ26፥1፤37፥20፤ 41፥55፤42፥5፤ ዘጸ28፥22፤ 2ሳሙ24፥13፤ 1ዜና21፥12፤ ኢዮ20፥16፤መዝ58፥4፤ 91፥6፤ኤር8፥17፤ አሞ5፥18-19፤ ሚክ7፥17 32፥25 2ዜና36፥17፤ ኢሳ13፥18፤24፥17፤ ኤር4፥31፤14፥18፤ ሰቆ1፥20፤2፥21፤ ሕዝ7፥15፤2ቆሮ7፥5 32፥26 ዘኍ14፥12፤ ዘጸ4፥27፤ኢዮ18፥17፤ መዝ18፥17፤34፥16፤ 37፥28፤109፥15፤ ኢሳ14፥20 32፥27 ዘጸ9፥26-28፤መዝ140፥8፤ ኢሳ10፥13፤ ኤር40፥2-3 32፥28 ኢሳ1፥3፤ 5፥13፤27፥11፤ ኤር8፥7 32፥29 ዘጸ5፥29፤ መዝ81፥13፤ ኢሳ47፥7፤ሰቆ1፥9 32፥30 ዘሌ26፥8፤ ዘኍ21፥34፤ 1ሳሙ12፥9፤23፥7፤ መሳ2፥14፤3፥8፤4፥2፤ 10፥7፤መዝ31፥8፤ 44፥12፤106፥41፤ ኢሳ50፥1፤ 54፥6 32፥31 ዘፍ49፥24፤ ዘፀ14፥25 32፥32 ዘጸ29፥18፤ ኢዮ6፥4፤20፥16፤ ኤር23፥14 32፥33 ቍ24 32፥34 ኢዮ14፥17፤ ኤር2፥22፤ሆሴ13፥12 32፥35 ቍ41፤ ዘፍ4፥24፤30፥2፤ ዘፀ32፥34፤መዝ17፥5፤ 35፥6፤37፥31፤38፥16፤ 54፥5፤66፥9፤73፥2፡18፤ 94፥18፤121፥3፤ ምሳ4፥19፤ኤር23፥12፤ 51፥6፤ሕዝ7፥8-9፤ ሮሜ12፥19፤ዕብ10፥30 32፥36 ዘሌ26፥43-45፤ዘጸ30፥1-3፤ መሳ2፥18፤1ነገ14፥10፤ 21፥21፤2ነገ9፥8፤ መዝ90፥13፤102፥13፤ 103፥13፤106፥45፤ 135፥14፤ኢዩ2፥14፤ አሞ7፥3፤ዕብ10፥30 32፥37 መሳ10፥14፤ ኤር2፥28፤11፥12 32፥38 ዘኍ25፥1-2፤ ኤር11፥12፤44፥8፡25 32፥39 ቍ12፤ዘፀ15፥26፤ዘጸ15፥26፤ 1ሳሙ2-6፤2ነገ5፥7፤ኢዮ5፥18፤9፥12፤ 10፥7፤15፥11፤መዝ7፥2፤ 47፥3፤ 50፥22፤68፥20፤ኢሳ6፥10፤19፥22፤30፥26፤41፥4፤43፥10፡13፤ 44፥7፤46፥4፤ 48፥12፤53፥5፤57፥18፤ኤር33፥6፤ዳን4፥35፤ሆሴ5፥14፤ 6፥1፤ሚል4፥2፤ዮሐ11፥25-26፤1ጴጥ2፥24 32፥40 ዘፍ14፥22፤ 21፥33፤ራእ1፥18 32፥41 ቍ35፤መሳ7፥20፤መዝ7፥12፤45፥3፤ 137፥8፤149፥7፤ኢሳ27፥1፤34፥6፤ 66፥16፤ኤር12፥12፤24፥56፤25፥14፤ 46፥10፤50፥29፤ 51፥24፡56፤ሕዝ21፥9-10፤ናሆ1፥2 32፥42 ቍ23፤ 2ሳሙ2፥26፤ኤር12፥12፤44፥1፤46፤10፡14 32፥43 2ነገ9፥7፤ መዝ65፥3፤79፥9፤ 137፥6፤ኢሳ1፥24፤25፥9፤ 65፥18፤66፥10፤ 33፥2 ዘፀ19፥18፤ ዘኍ10፥12፤ኢሳ11፥17፤መሳ5፡4፤ መዝ50፥2፤68፥8፤ 80፥1፤89፥7፤94፥1፤ ዳን4፥13፤ 7፥10፤8፥13፤ዘካ14፥5፤ ሐሥ7፥53፤ገላ3፥19፤ዕብ2፥2፤ራእ5፥11፤ኤር9፥9፤ሮሜ15፥10፤ራእ6፥10፤

[ሀ]43 ወይም፣ ሕዝቦች ሆይ፤ ደስ ይበላችሁ።
[ለ]43 የማሶሬቱ ቅጅ፣ የሙት ባሕር ጥቅል እንዲሁም የሰብዓ ሊቃናት ትርጉም፣ ሕዝቦች ሆይ፤ መላእክት ሁሉ ለእርሱ ይስገዱ ይላሉ።

የእስራኤል ሕዝቦች የሚጠሩበት ሌላው ስም ነው። ከዚህም በተጨማሪ ኢሳ 44፥2 እና ማብ ይመ። *መጠጊያ ዐለት፤* ቍ18 ይመ፤ የቍ 4 ማብ ይመ።

*32፥21፤* እስራኤላውያን ስለ ክርስቶስ የተነገራቸውን የምሥራች ቃል መረዳት ያቃታቸው መሆኑን ለመግለጽ በሮሜ 10፥19 ላይ በከፊል ተጠቅሶ ይገኛል።

32፥22 *እስከ ሲኦል ዘልቆ፤* የዘፍ 37፥35 ማብ ይመ።

32፥30 *መጠጊያ ዐለታቸው፤* የእስራኤልን አምላክ ለማለት ነው።

32፥31 *የእነርሱ መጠጊያ ዐለት፤* የእስራኤልን ጠላቶች አማልክት ለማለት ነው።

32፥34 *በመዝገቤስ የታተመ፤* እግዚአብሔር ወደፊት የሚያደርጋቸው ነገሮች ሁሉ፣ አስቀድሞ የተወሰኑ ናቸው፤ ደግሞም በተወሰነው መሠረት ይፈጸማሉ። ኀጢአትም በጊዜው ይቀጣል።

*32፥35-36፤* የእግዚአብሔርን ልጅ አለመቀበል የሚያስከትለውን ቅጣት ለማመልከት በዕብ 10፥30 ላይ በከፊል ተጠቅሶአል።

32፥35 *በቀል የእኔ ነው፤ እኔ ብድራትን እመልሳለሁ፤* በቀል የእግዚአብሔር ልዩ ሥልጣን መሆኑን ለማረጋገጥ በሮሜ 12፥19 ላይ ተጠቅሶአል።

32፥39 *ከእኔም በቀር ሌላ አምላክ የለም፤* የ4፥35 ማብ ይመ።

እርሱ የአገልጋዮቹን ደም ይመልሳል፤
ጠላቶቹንም ይበቀላል።
ምድሪቱንና ሕዝቡን ይቤዣቸዋልና።

[44]ሙሴም ከነዌ ልጅ ከኢያሱ ጋር መጥቶ የዚህን መዝሙር ቃሎች በሕዝቡ ጆሮ ተናገረ። [45]ሙሴም እነዚህን ቃሎች ሁሉ ለመላው እስራኤል ተናግሮ ከጨረሰ በኋላ፣ [46]እንዲህ አላቸው፤ የዚህን ሕግ ቃሎች ሁሉ በጥንቃቄ ይጠብቁ ዘንድ ልጆቻችሁን እንድታዝዟቸው፣ እኔ ዛሬ በግልጥ የምነግራችሁን ቃሎች ሁሉ በልባችሁ አኑሩ። [47]ቃሎቹ ለእናንተ ሕይወታችሁ እንጂ እንዲሁ ባዶ ቃሎች አይደሉም፤ በእነርሱ የዮርዳኖስን ተሻግራችሁ፤ በምትወርሷትም ምድር ረጅም ዘመን ትኖራላችሁ።

### ሙሴ በናባው ተራራ ላይ መሞቱ

[48]በዚያችም ዕለት እግዚአብሔር (ያህዌ) ሙሴን እንዲህ አለው፤ [49]ከኢያሪኮ ማዶ ባለው የሞዓብ ምድር፣ ከዓባሪም ተራሮች አንዱ ወደ ሆነው ወደ ናባው ተራራ ወጥተህ ለእስራኤላውያን ርስት አድርጌ የምሰጣትን የከነዓንን ምድር አሻግረህ ተመልከት። [50]ወንድምህ አሮን በሖር ተራራ ላይ እንደ ሞተና ወደ ወገኖቹ እንደ ተሰበሰበ ሁሉ፣ አንተም በወጣህበት በዚያ ተራራ ላይሙት፤ ወደ ወገኖችህም ተሰብሰብ። [51]ይህ የሚሆንበት ምክንያት ሁለታችሁም በጺን ምድረ በዳ፣ ቂቃዴስ በመሪባ ውሃ አጠገብ በእኔ ላይ መታመናችሁን በእስራኤላውያን ፊት ስላጐደላችሁና ቅድስናዬንም በእስራኤላውያን መካከል ስላላከበራችሁ ነው። [52]ስለዚህ ምድሪቱን ከሩቅ ሆነህ ታያታለህ እንጂ፣ ለእስራኤል ሕዝብ ወደምሰጣት ምድር አትገባም።"

### ሙሴ የእስራኤልን ነገዶች ባረከ

33፥1-29 ማመ - ዘፍ 49፥1-28

**33** የእግዚአብሔር (ያህዌ) ሰው ሙሴ ከመሞቱ በፊት ለእስራኤላውያን የሰጠው ቃለ ቡራኬ ይህ ነው፤ [2]እንዲህም አለ፦
"እግዚአብሔር (ያህዌ) ከሲና መጣ፤
በእነርሱም ላይ ከሴይር እንደ ማለዳ ፀሐይ
ወጣ፤
ከፋራን ተራራ አበራላቸው፤
ከአእላፋት ቅዱሳኑ ጋር⁺ መጣ፤
በስተቀኙ የሚነድ እሳት ነበር።
[3]በእርግጥ ሕዝቡን የምትወድ አንተ ነህ፤
ቅዱሳኑ ሁሉ በእጅህ ውስጥ ናቸው።
ከእግርህ ሥር ሁሉ ይሰግዳሉ፤
ከአንተ ትእዛዝ ይቀበላሉ፤
[4]ይህ ሙሴ የሰጠን ሕግ፣
የያዕቆብ ጉባኤ ርስት ነው።
[5]የሕዝቡ አለቆች ከእስራኤል ነገዶች ጋር
ሆነው፣
በአንድነት በተሰበሰቡ ጊዜ፣
እርሱ በይሹሩን[a] ላይ ንጉሥ ነበር።
[6]"ሮቤል በሕይወት ይኑር፤ አይሙት፤
የወገኖቹ ቍጥርም አይጕደልበት።"
[7]ስለ ይሁዳ የተናገረው ይህ ነው፦
"እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤ የይሁዳን ጩኸት
ስማ፤
ወደ ወገኖቹም አምጣው።
በገዛ እጆቹ ራሱን ይከላከላል፤
አቤቱ ከጠላቶቹ ጋር ሲዋጋ ረዳቱ ሁን!
[8]ስለ ሌዊም እንዲህ አለ፦
"ቱሚምህና ኡሪምህ፣
ለምትወደው ሰው ይሁን፤
ማሳህ በተባለው ቦታ ፈተንኸው፤
በመሪባም ውሃ ከእርሱ ጋር ተከራከርህ።
[9]ስለ አባቱና ስለ እናቱ ሲናገርም፣
'ስለ እነርሱ ግድ የለኝም' አለ።
ወንድሞቹን አላለያቸውም፤
ልጆቹንም አላወቃቸውም። ለቃልህ ግን
ጥንቃቄ አደረገ፤
ኪዳንህንም ጠበቀ።
[10]ሥርዐትህን ለያዕቆብ፣
ሕግህንም ለእስራኤል ያስተምራል።
ዕጣን በፊትህ፣
የሚቃጠለውን መሥዋዕት ሁሉ በመሠዊያህ
ላይ ያቀርባል።
[11]እግዚአብሔር (ያህዌ) ሆይ፤ ኀይሉን ሁሉ ባርክለት፤
በእጁ ሥራ ደስ ይበልህ፤
በእርሱ ላይ የሚነሡበትን ሽንጣቸውን ቍረጠው፤
ጠላቶቹንም እንዳያንሠራሩ አድርገህ
ምታቸው።"

32፥44 ዘኍ13፥8፡16
32፥46 ዘዳ6፥6፡7፤ ዮሐ1፥17፤7፥19
32፥47 ዘፀ23፥26፤ ዘዳ30፥20፤ 33፥25፤ ኢሳ65፥22
32፥48 ዘኍ27፥12
32፥49 ዘሌ14፥34፤ ዘኍ22፥1፤27፥12፤ 32፥3
32፥50 ዘፍ25፥8፤ ዘኍ20፥22፡29፤ 27፥13
32፥51 ዘኍ13፥21፤ 20፥11-13፤27፥14፤ ሕዝ47፥19
32፥52 ዘዳ3፥37፤ 34፥1-3
33፥1 ዘፍ27፥4፤ ኢሱ14፥6፤1ሳሙ2፥27፤ 9፥6፤1ነገ12፥22፤ 13፥1፤2ነገ1፥9-13፤ 5፥8፤ኤር35፥4
33፥3 ዘዳ4፥37፤ 7፥6፤ሉቃ10፥39፤ ራእ4፥10
33፥4 ዘዳ4፥2፤ ዮሐ1፥17፤7፥19፤ መዝ119፥11
33፥5 ዘፀ16፥8፤ ዘኍ23፥21፤ዘዳ32፥15፤ 1ሳሙ10፥19፤ መዝ10፥16፤149፥2
33፥6 ዘፍ34፥5
33፥7 ዘፍ49፥10
33፥8 ዘፍ29፥34፤ ዘፀ17፥7፤28፥30፤ ዘኍ14፥22፤ መዝ106፥16
33፥9 ዘፀ32፥26-29፤ መዝ61፥5፤ሚል2፥5
33፥10 ዘፀ30፥7፤ ዘሌ10፥11፤16፥12-13፤ ዘዳ17፥8-11፤31፥9-13፤ ዕዝ7፥10፤ነህ8፥18፤ መዝ119፥151፤ ኤር23፥22፤ሚል2፥6፤ መዝ51፥19
33፥11 2ሳሙ24፥23፤ መዝ20፥3፤51፥19

⁺2 ወይም *በአእላፋት ቅዱሳኑ።*
[a]5 በዚህ ስፍራና በቍጥር 26 ላይ ይሹሩን ማለት፣ *ቅን ወይም ትክክለኛ* ማለት ሲሆን ይኸውም እስራኤልን የሚያሳይ ነው።

*አገድላለሁ፤ ... እፈውሳለሁም፤* ኢሳ 45፥7 እና ማብ ይመ።

32፥43 *አሕዛብ ሆይ፤* ከሕዝቡ ጋር ደስ ይበላችሁ፤ በሙት ባሕር አካባቢ የተገኙ ቅጆች በዚህ ቍጥር ላይ፣ "የእግዚአብሔር መላእክት ሁሉ ይስገዱለት" የሚል ተጨማሪ ሐረግ የያዙ ሲሆን፣ ይህም ሐረግ በዕብ 1፥6 ላይ ተጠቅሶአል።

32፥47 *ሕይወታችሁ፤* የ30፥20 ማብ ይመ።

32፥50 *አሮን በሖር ተራራ ላይ እንደ ሞተ፤* 10፥6፤ ዘኍ 20፥22-29 ይመ። *ወደ ወገኖቹ እንደ ተሰበሰበ፤* የዘፍ25፥8 ማብ ይመ።

32፥51 *በጺን ምድረ በዳ፣ በቃዴስ መሪባ፤* 33፥8 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 17፥7፤ የዘኍ 20፥13 ማብ ይመ። *በእኔ ላይ ያላችሁን እምነት ... ስላጐደላችሁ፤* 1፥37፤ 3፥23-26፤ 4፥21-22፤ 31፥2፤ ዘኍ 20፥12 ይመ።

33፥1 *የእግዚአብሔር ሰው፤* ይህ ስያሜ ለመጀመሪያ ጊዜ የተጠቀሰው በዚህ ስፍራ ነው። ከዚህም በኋላ በኢሱ 14፥6 ላይ ሙሴን አስመልክቶ ተጠቅሶአል (የመዝ 90 ርእስ ይመ)። በኋላም ሌሎችን የእግዚአብሔር መልእክተኞች ለማመልከት ተጠቅሶአል (የ1ሳሙ 2፥27 ማብ ይመ)። *ቃለ ቡራኬ፤* ዘፍ 12፥1-3፤ 22፥15-18፤ 27፥27-29፤ 28፥10-15፤ 49፥1-28 ይመ። ሙሴ የእስራኤልን ነገዶች ሲባርክ የተናገረውን ቃል (ቍ6-25) ያዕቆብ በዘፍ 49 ላይ ልጆቹን ሲባርክ ከተናገረው ቃል ጋር ማነጻጸር አስፈላጊ ነው።

33፥2 *ሲና ... ሴይር ... ፋራን፤* ሕጉ የተሰጠባቸው ተራሮች ናቸው (ዘፍ 21፥21 እና ማብ፤ መሳ 5፥4-5፤ ዕን 3፥3 ይመ)። *ከአእላፋት ቅዱሳኑ፤* መላእክቱን ለማለት ነው።

33፥3 *ቅዱሳኑ፤* እስራኤላውያንን ለማለት ነው (7፥6፤ 14፥2፤ 26፥19፤ 28፥9 ይመ)።

33፥5 *ይሹሩን፤* የ32፥15 ማብ ይመ። *ንጉሥ ነበር፤* በእስራኤል ላይ መንገሥ የሚገባው እግዚአብሔር እንጂ ምድራዊ ገዥ አይደለም (መሳ 8፥23 እና ማብ ይመ)።

33፥8 *ቱሚምህና ኡሪምህ፤* የዘጸ 28፥30 ማብ ይመ። *ማሳህ፤* 6፥16፤ 9፥22፤ ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 17፥7 ማብ ይመ። *መሪባ፤* 32፥51 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ 17፥7 ማብ ይመ።

33፥9 *ለቃልህ ግን ጥንቃቄ አደረገ፤* ሌዋውያን፣ የመገናኛውን ድንኳንና የሕጉ መጽሐፍ የተቀመጠበትን ታቦት የመጠበቅ ኀላፊነት ነበረባቸው (የ31፥9 ማብ ይመ)።

33፥10 *ሥርዐትህን ለያዕቆብ ... ያስተምራል፤* የ31፥11 ማብ ይመ።

# መጽሐፈ ሩት

## መግቢያ

### የመጽሐፉ አሰያየም

መጽሐፉ የተሰየመው ከመጽሐፉ ገጸ ባሕርያት አንዷ በሆነችው በዳዊት የሴት ቅድመ አያትና በኢየሱስ የጥንት የትውልድ ሐረግ ውስጥ ባለችው (ማቴ1፥1:5) በሞዓባዊቷ ሴት በሩት ስም ነው:: በመ ጽሐፍ ቅዱስ ከተጻፉት መጻሕፍት በሴት ስም ርእስ የተሰጠው ሌላው መጽሐፍ የአስቴር መጽሐፍ ነው::

### ታሪካዊ ዳራው

ታሪኩ በመሳፍንት ዘመን ሃይማኖት ወይም እግዚአብሔርን መፍራት በጠፋበትና የሥነ ምግባር ብልሹነት በበዛበት፣ የአገር አንድነት በፈረሰበትና የባዕዳን አገሮች ጭቈና በተንሰራፋበት ጊዜ የተከናወነ ነው:: መጽሐፈ ሩት በእስራኤልና በሞዓብ መካከል ለጥቂት ጊዜ የነበረውን ሰላም ያመለክታል (ከመሳ 3፥12-20 ጋር ያነጻጽሩ):: መጽሐፉ እንደ 1ሳሙ 1-2፣ የአንድን እስራኤላዊ ቤተሰብ የግል ሕይወት ሁኔታ፣ በተጨማሪም በመሳፍንት ዘመን እውነተኛ እምነትና እግዚአብሔርን የመፍራት ሕይወት የነበ ራቸው ጥቂት ሰዎች በዘመኑ የነበረውን ጨለማ እንዴት እንዳቃለሉ የሚያመለክት አስገራሚ ትረካ ያቀርባል::

### ጸሓፊውና የተጻፈበት ጊዜ

ጸሓፊው ማን እንደሆነ በትክክል አይታወቅም:: በአይሁድ ትውፊት የመጽሐፉ ጸሓፊ ሳሙኤል እንደሆነ ቢነገርም፣ የዳዊት ስም በመጠቀሱ (4፥17:12) ወደ ኋላ የነበረውን ዘመን ስለሚያመለክት ሳሙኤል ሊጽፈው አይችልም የሚል ግምት አለ:: በዚህ መጽሐፍ የቀረበው የዕብራውያኑ የአጻጻፍ ዘዬ በነገሥታት ዘመን እንደ ተጻፈ ይጠቍማል::

### መሪ ሐሳቡና ትምህርተ መለኮቱ

ጸሓፊው ያተኰረው ሩት ለብቸኛዋ ለኑኃሚን በነበራት የማይናወጥና ከግለኝነት የራቀ መሰጠት (1፥16-17፤2፥11-12፤3፥10፤4፥5) እንዲሁም በዔዝ ለእነዚህ ባልቴቶች ባሳየው በጎነት ላይ ነው (ም2-4):: እንዲህ ያለው ፍቅር የሰውን ሥራ ከእግዚአብሔር ሥራ ጋር በማገናዘብ የእግዚአብሔርን ፍቅር ያንጸባ ርቃል (2፥12 እና 3፥9 ያነጻጽሩ):: እነዚህ ሰዎች ከእግዚአብሔር በጎነት የተነሣ ተባርከዋል፤ ለሌሎችም በረከት ሆነዋል::

የእግዚአብሔርን ፍቅር በግልጽ ሁኔታ የምታንጸባርቀው ይህች ሴት ሞዓባዊት መሆኗ የሚያስ ገርም ይመስላል ("መጽሐፈ ሩት" የሚለውን ካርታ ከገጽ ይመ):: ሩት በጋብቻ ለተቀላቀለችበት እስ ራኤላዊ ቤተ ሰብ ባሳየችው ፍጹም ታማኝነትና ብቻዋን ላለችው አማቷ ባላት ሙሉ መሰጠት እንደ እውነተኛ የእስራኤል ልጅ ሆና በመቈጠሯ፣ በዳዊት ዘር ግንድ ውስጥ ለመግባት ብቁ ሆና ተገኝታለች:: በሚመጣው የእግዚአብሔር መንግሥት ውስጥ መግባት የሚቻለው በዝምድና ወይም በደም ግንኙነት ሳይሆን "በእምነት አማካይነት ወደሚገኘው መታዘዝ" (ሮሜ1፥5) በሚለው ቃል አ ማካይነት የአንድ ሰው ሕይወት ከእግዚአብሔር ፈቃድ ጋር ሲስማማ ብቻ እንደሆነ የዚህች ሴት ሕ ይወት በምስክርነት ቀርቦአል:: በዳዊት የዘር ግንድ ውስጥ መግባቷ፣ ሕዝቦች ሁሉ በታላቁ የዳዊት ልጅ መንግሥት ውስጥ መወከላቸውን ያመለክታል::

በዳዊት የትውልድ ሐረግ ታሪክ ውስጥ አንዱ ክፍል እንደ መሆኑ፣ በድነት ታሪክ ውስጥ ዳዊት ያለውን ሚና ያመለክታል:: የትረካው ዋና ሐሳብ ሆኖ የሚታየው ድነት ሲሆን፣ ቃሉም በተለያየ መልኩ 23 ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል:: መጽሐፉ በቀዳሚነት ራሳቸውን በሰጡና እግዚአብሔር በባረካቸው በሩትና በቦዔዝ መልካም ተግባር የኑኃሚን ተስፋ መቍረጥ ወደ ደስተኛነት መለወጡን የሚተርክ ነው:: ኑኃሚን ያለችበት ሁኔታ ከባዶነት ወደ ሙላት (1፥21፤ 3፥17፤ የ1፥1:3:5-6:12:21-22፤ 3፥17፤ 4፥15 ማብ ይመ)፣ ከኵስቍልና ወደ ድነትና ተስፋ ወደ ማግኘት ተለውጦአል (4፥13-17)፤ 1፥1-5):: በተመሳሳይ መልኩ የእስራኤል ሕዝብ በዔሊ መሞት ምክንያት የነበረው ተስፋ መቍረጥ (1ሳሙ4፥18)፣ የሩትና የቦዔዝ እውነተኛ ልጅ በሆነው በዳዊት ራስን የመስጠት አገልግሎት አማካይነት በሰሎሞን ዘመን የመጀመሪያ ዓመታት ወደ ሰላምና ብልጽግና ተለውጦአል (1ነገ4፥20-34፤5፥4):: ጸሓፊው፣ የዳዊት ቤት በእስራኤል መንገሡ የእግዚአብሔር የቸርነት አገዛዝ እንደ መሆኑ መጠን እግዚአብሔር የገባውን ቃል ሰላምና ዕረፍት በመሥጠት መፈጸሙን የሚያመለክት ነው:: ይህ ዕረፍት ቀጣይነት የሚኖረው በዚህ መንግሥት ውስጥ ያሉ ሁሉ በዕለት ኑሮአቸው በሩትና በቦዔዝ ሕይወት የታየውን ራስን የመስጠት ፍቅር ሲከተሉ ወይም ሲያሳዩ ብቻ ነው:: ታላቅ በሆነው "የዳዊት ልጅ"(ማቴ1፥1) በኢየሱስ እና በእርሱ የማዳን ሥራ በእግዚአብሔር መንግሥት ቃል የተገቡት በረከቶች ፍጻሜ አግኝተዋል::

### ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ

መጽሐፈ ሩት ፍጹም በሆነ ጥበብ የተዘጋጀ የዕብራውያን አጭር ታሪክ ነው:: በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ካሉት የታሪክ መጻሕፍት መካከል በግልጽነት፣ በተነባቢነትና በሥነ ጽሑፍ ውበት ከሩት የሚበልጥ የለም::

ይህም የዕብራውያን የጽሑፍ ጥበብ አሸብርቆ የታየበት መጽሐፍ ነው።
ይህ ታሪክ በአራት የተከፈለ ሲሆን፣ ከተስፋ መቍረጥ ትረካ ይጀምርና (1፥1-5፥7)፣ አጠር ወዳለ የዕረፍትና ተስፋ የማግኘት ትረካ ይሄዳል (4፥13-17)። በዕብራይስጡ ማለትም ተስፋ መቍረጥና ተስፋ ማግኘት በሁለቱም ክፍሎች እኩል የሆነ የቃላት ብዛት አለው። ዋነኛው የለውጡ ስፍራ በመጽሐፉ እኩሌታ ላይ ይገኛል (የ2፥20 ማብ ይመ)። የአራቱም ክፍሎች የመግቢያ ዐረፍተ ነገሮች ዋና ሐሳቡን ፈንጠቅ ያደርጋሉ (1፥6 መመለስ፤ 2፥1 ከቦዔዝ ጋር መገናኘት፤ 3፥1 ለሩት ቤት መፈለግ፤ 4፥1 በከተማው መግቢያ በር የተፈጸመው ወሳኝ ክስተት)። የእያንዳንዱ ክፍል የመዝጊያ ዐረፍተ ነገሮች ደግሞ ወደሚቀጥለው ክፍል ለመግባት መንገድ ያመቻቻሉ (የ1፥22፤ 2፥23፤ 3፥18 እና 4፥12 ማብ ይመ)። አንዳንድ ቃላትም በንጽጽር ተቀምጠዋል፤ ጣፋጭ (የኑኃሚን ትርጉም) እና መራራ (1፥20)፣ ሙሉ እና ባዶ (1፥21)፣ ሕያውና ሙት (2፥20)። ከሁሉም የሚያስደንቀው በሁለቱ ገጸ ባሕርያት (በሩትና በቦዔዝ) መካከል ያለው ንጽጽር ነው። ይህም አንደኛዋ ወጣት፣ እንግዳ፣ ብቸኛና መበለት ስትሆን፣ ሌላኛው ሰው በመካከለኛ ዕድሜ የሚገኝ፣ በቤቱና በኅብረተሰቡ መካከል ያለችግር የሚኖር እስራኤላዊ ነው። ለሁለቱም፣ በጎነታቸው አጉልተው የሚያሳዩ ተዛማጅ ወገኖች አሉ፤ ለሩት--ዖርፋ፣ ለቦዔዝ--ስሙ ያልተጠቀሰው የአቤሜሌክ ዘመድ።

የመጽሐፈ ሩት ጸሓፊ፣ አንባቢዎቹ የታሪኩ ዋና ሐሳብ ከሆነው በሩትና በቦዔዝ መልካም ተግባር እማ ካይነት ከባዶነት ወደ ሙላት ከተለወጠው የኑኃሚን ሕይወት እንዳይርቁ ጥንቃቄ ያደርጋል። ለውጡ ወይም መልሶ መቋቋሙ በመጀመሪያ የተፈጸመው ከሞዓብ ምድር ወደ ተስፋዪቱ ምድር ወደ ቤተልሔም ከመመለስ ጋር የተያያዘ ነው ("የዳቦ ቤት" የ1፥1 ማብ ይመ)። በመቀጠልም የምድሪቱ አዝመራ የሚሰበሰብበት የመከር ጊዜን ያመለክታል። የታሪኩ ገጽታዎች በሙሉ የአንባቢውን ትኵረት በዋነኛው ጉዳይ ላይ እንዲሆን ያደርጋል። እነዚህና በጥናት ጽሑፉ ውስጥ የተጠቀሱት ሌሎች ሐሳቦች መጽሐፈ ሩትን ለመረዳት አጋዥ ይሆናሉ።

***አስተዋፅኦ***

1. መግቢያ፤ የኑኃሚን ለብቻ መቅረት (1፥1-5)
2. የኑኃሚን ከሞዓብ ምድር መመለስ (1፥6-22)
    ሀ. ሩት ወደ ኑኃሚን ተጠጋች (1፥6-18)
    ለ. የሩትና የኑኃሚን ወደ ቤተ ልሔም መመለስ (1፥19-22)
3. የሩትና ቦዔዝ በዕርሻ ስፍራ መገናኘት (ም2)
    ሀ. ሩት ሥራ መጀመሯ (2፥1-7)
    ለ. ቦዔዝ ለሩት ቸርነት ማድረጉ (2፥8-16)
    ሐ. የሩት ወደ ኑኃሚን መመለስ (2፥17-23)
4 ቦዔዝና ሩት በዐውድማው ላይ (ም3)
    ሀ. ኑኃሚን ሩትን የመከረቻት ምክር (3፥1-5)
    ለ. ቦዔዝ ሩትን ለመዋጀት ቃል መግባቱ (3፥6-15)
    ሐ. የሩት ወደ ኑኃሚን መመለስ (3፥16-18)
5. ቦዔዝ ሩትን ለማግባት ሁኔታዎችን ማመቻቸቱ (4፥1-12)
    ሀ. ቦዔዝ የመዋጀት መብት ያለውን የሥጋ ዘመዱን ማነጋገሩ (4፥1-8)
    ለ. ቦዔዝ የኑኃሚንን ንብረት መግዛቱና ሩትን ማግባቱ (4፥9-12)
6. ማጠቃለያ፤ የኑኃሚን ኑሮ መሟላት (4፥13-17)
7. መደምደሚያ፤ የዳዊት ትውልድ ሐረግ (4፥18-22)

## ኑኃሚንና ሩት

1 መሳፍንት[ሠ] በሚገዙበት ዘመን፣ በምድሪቱ ላይ ራብ ሆነ፤ አንድ ሰው በይሁዳ ከምትገኘው ከቤተ ልሔም ሚስቱንና ሁለቱን ወንዶች ልጆቹን ይዞ ለተወሰነ ጊዜ ለመኖር ወደ ሞዓብ አገር ሄደ። [2]የሰውየው ስም አቤሜሌክ፣ የሚስቱ ኑኃሚን፣ የሁለቱም ወንዶች ልጆቹ ስሞች መሐሎንና ኬሌዎን ነበሩ:: እነርሱም የይሁዳ ቤተ ልሔም ኤፍራታውያን ሲሆኑ፣ ወደ ሞዓብ አገር ሄደው በዚያ ኖሩ::

[3]የኑኃሚን ባል አቤሜሌክ ሞተ፤ ኑኃሚንም፣ ከሁለት ልጆቿ ጋር ብቻዋንቀረች:: [4]ልጆቿም ዖርፋና ሩት የተባሉ የሞዓብ ሴቶችን አገቡ፤ በዚያም ዐሥር ዓመት ያህል ከኖሩ በኋላ፣ [5]መሐሎንና ኬሌዎን ሁለቱም ሞቱ፤ ኑኃሚንም ሁለት ልጆቿንና ባሏን አጥታ ብቻዋን ቀረች::

[6]እርሷም በሞዓብ ሳለች እግዚአብሔር ሕዝቡን እንደ ጐበኘና እህል እንደ ሰጣቸው በሰማች ጊዜ፣ ሁለቱን ምራቶቿን ይዛ ወደ አገሯ ለመመለስ ከዚያ ተነሣች:: [7]የኖረችበትን ስፍራ ትታ ከሁለቱ ምራቶቿ ጋር ወደ ይሁዳ ምድር የሚመልሳቸውን መንገድ ይዘው ጒዞአቸውን ቀጠሉ::

[8]ከዚያም ኑኃሚን ሁለቱን ምራቶቿን እንዲህ አለቻቸው፤ "እያንዳንዳችሁ ወደ እናቶቻችሁ ቤት ተመለሱ፤ ለሞቱ ባሎቻችሁና ለእኔ በጎ ነገር እንዳደረጋችሁ፣ ለእናንተም እግዚአብሔር እንደዚሁ ያድርግላችሁ፤ [9]እያንዳንዳችሁ በምታገቡት ባል ቤት፣ እግዚአብሔር ያሳርፋችሁ::"

ከዚያም ሳመቻቸው፤ እነርሱም ድምፃ

1፥1 ዘፍ12፥10፤ 35፥19፤36፥35፤ 47፥4፤መሳ2፥16-18፤ 2፥16፥25፤ መዝ105፥16፤ሐጌ1፥11
1፥2 ቍ3:5፤ ዘፍ35፥16:19፤ ሩት2፥1፥4፥3፤ 1ሳሙ16፥18
1፥4 ቍ14፤ ሩት4፥13፤1ነገ11፥1፤ 2ዜና24፥26፤ዕዝ9፥2፤ ነህ13፥23፤ማቴ1፥5
1፥5 ቍ2:8፤ ሩት2፥11
1፥6 ዘፍ11፥31፤ 36፥35፤38፥16፤ 50፥24፤ዘፀ4፥31፤ መዝ132፥15፤ ኤር29፥10፤ሶፎ2፥7፤ ማቴ6፥11
1፥8 ቍ5፤ዘፍ19፥19፤ 38፥11፤2ጢሞ1፥16
1፥9 ዘፍ27፥27:38፤

[ሠ]1 በትውፊት ፈራጆች ተብሉአል::

1፥1 *መሳፍንት በሚገዙበት ዘመን፤* ይህ የሆነው ምናልባት ከ1380-1050 ዓ.ቅ.ክ ባሉት ዓመታት ውስጥ ነው (ከመጽሐፈ መሳፍንት መግቢያ "ዳራ" የሚለውን ይመ):: ጸሓፊው የመሳፍንትን ዘመን የጠቀሰበት ምክንያት እስራኤል በክህደት፣ በሥነ ምግባር ዝቅጠትና በጭቈና ውስጥ የነበረችበትን ዘመን ለማስታወስ ነው:: *ራብ፤* ይህ በመሳፍንት መጽሐፍ ውስጥ አልተጠቀሰም:: *በይሁዳ... ቤተ... ልሔም፤* የዳዊት ከተማ ናት (1ሳሙ16፥18):: *ቤተ ልሔም፤* (የስሙ ትርጒም "የምግብ ቤት" ማለት ነው) ባደ ናት::

1፥2 *አቤሜሌክ፤* "አምላኬ ንጉሥ ነው" ማለት ነው (የመሳ 8፥23 ማብ ይመ)፤ *ኑኃሚን፤* "አስደሳች" ማለት ነው (ቍ 20 ይመ)፤ *ኤፍራታውያን፤* ኤፍራታ በቤተ ልሔም ዙሪያ ለሚገኘው አካባቢ የተሰጠ ስም ነው (4፥11፤ዘፍ 35፥19፤ 1ሳሙ 17፥12፤ ሚክ 5፥2 ይመ)::

1፥3 *የኑኃሚን ባል አቤሜሌክ ሞተ፤* የኑኃሚን ባዶ እጇን መቅረት ከዚህ ይጀምራል (ቍ21 ይመ)::

1፥4 *ሩት፤* ይህ ስም "ወዳጅነት" የሚል ትርጒም የሚሰጠውን የዕብራይስጡን ቃል ድምፅ ይመስላል:: ሩት በማቴዎስ ወንጌል ላይ በኢየሱስ ክርስቶስ የትውልድ ሐረግ ስማቸው ከተጠቀሰው አራት ሴቶች አንዷ ናት፤ ሌሎቹ ሴቶች ትዕማር፣ ረዓብና ቤርሳቤህ ናቸው (ማቴ 1፥3:5-6 ይመ):: *የሞዓብ ሴቶችን፤* ዘፍ19፥36-37 ይመ፤ የሞዓባውያን ሴቶች ማግባት አልተከለከለም፤ ነገር ግን አንድ ሞዓባዊ ወይም እስከ 0ሥር ትውልድ ድረስ ያሉት ልጆቹ "ወደ እግዚአብሔር ጉባኤ" መግባት አይፈቀድላቸውም ነበር (ዘዳ 23፥3):: *አገቡ፤* ዘርን ማስቀረት የተለመደ ነው::

1፥5 *መሐሎን፤* የሩት ባል ነው (4፥10 ይመ):: *ኑኃሚን ... ብቻዋን ቀረች፤* ኑኃሚን ባዶ እጇን ቀረች፤ ባሏንም፣ ልጆቿንም አጣች፤ የስሙ ትርጒም "ደካማ" ማለት ሊሆን ይችላል:: አሁን አብረዋት ያሉት የሟች ልጆቿ ሚስቶች ሲሆኑ እነርሱም ያልወለዱና መጻተኞች ነበሩ::

1፥6 *እግዚአብሔር ሕዝቡን እንደ ጐበኘና እህል እንደሰጣቸው፤* በታሪኩ ውስጥ ብዙ ቦታ ላይ እግዚአብሔር የታሪክ ባለቤት መሆኑ በግልጽ ተጠቅሶአል (ቍ13:21፤ 2፥20፤ 4፥12-15):: እህል ቤተ ልሔም ("የምግብ ቤት") እንደ ገና ምግብ አገኘች:: *ለመመለስ ከዚያ ተነሣች፤* ባዶዋን የቀረችው ኑኃሚን አሁን እህል በእህል ወደ ሆነችው ወደ ተስፋዪቱ ምድር ተመለሰች::

1፥8 *ተመለሱ፤* ምስኪኗ ኑኃሚን የልጆቿ ሚስቶች ወደ አገራቸው ወደ ሞዓብ እንዲመለሱ ደጋግማ ለመነቻቸው (እዚህ ላይ ቍ11-12:15 ይመ)፤ ይህን ያደረገችውም የምትሰጣቸው ምንም ነገር ስላልነበራት ነው:: *በጎ ነገር ...፤* 2፥20፤ 3፥19 ይመ::

## መጽሐፈ ሩት

ጨለማና ደም መፋሰስ በበዛበት በመሳፍንት ዘመን ውስጥ የተፈጸመው የሩት ታሪክ በአይሁዳውያንና በሞአባውያን ሕዝቦች መካከል ያለውን ግጭትና የኀሪጥ መተያየት በዝምታ አልፎታል:: አንድ ጊዜ የሞአባውያን በነበሩት ከተሞች ላይ የእስራኤል ነገዶች ያደረጉት ወረራ የተዘነጋ ወይም ይቅር የተባለ አልነበረም:: የዕብራውያን ነቢያት፣ ሞአብ በእስራኤል ላይ የሞከረውን ሚርት፣ ጭቆናና ማታለል፣ የትዕቢትና የእብሪት ሥራውን ሁሉ ተቃውመዋል:: የሜሻ ሐውልት (830 ዓ.ቅ.ክ) የእስራኤልን ከተሞች ሁሉ መጨፍጨፍ ያወራል::

የሞአብ ምድር በሙት ባሕር ባለው ሰፊ ሜዳማ ስፍራና በምሥራቅ በሁለት ታላላቅ ስምጥ ሸለቆዎች መካከል ያለውን በረሃ ያጠቃልላል:: በምሥራቅ ያለው ምድር በጣም ተራራማ ስለሆነ ለበጎችና ለፍየሎች ግጦሽ በስተቀር ለእርሻ የሚሆን መሬት የለውም:: በአካብ ዘመን ከሞአብ ይመጣ የነበረው ግብር 100.000 በጎች ጸጉር ነበር::



ቸውን ከፍ አድርገው አለቀሱ፤ [10]ቀጥለውም፣ “አይሆንም! ከአንቺ ጋር ተመልሰን ወደ ወገ ኖችሽ እንሄዳለን” አሏት።

[11]ኑኃሚን ግን እንዲህ አለቻቸው፤ “ልጆቼ ሆይ፤ ወደየቤታችሁ ተመለሱ፤ ከእኔ ጋር ለምን ትሄዳላችሁ? ባል የሚሆኗችሁ ሌሎች ልጆች ከእንግዲህ የምወልድ ይመስላችኋልን? [12]ወደየቤታችሁ ተመለሱ ልጆቼ፤ ሌላ ባል እንዳላገባ እጅግ አርጅቻለሁ፤ አሁንም ተስፋ አለኝ ብል፣ ዛሬ ማታ አግብቼ ከዚያም ልጆች ብወልድ፣ [13]እስኪያድጉ ድረስ ትጠብቃላችሁን? እነርሱን በመጠበቅ እስከዚያ ሳታገቡ ትቈያላችሁን? ልጆቼ ሆይ፤ እንዲህ አይ ሆንም፤ ሁኔታው ከእናንተ ይልቅ ለእኔ እጅግ መራራ ነው፤ *የእግዚአብሔር* እጅ በእኔ ላይ ወጥቶአልና።”

[14]እነርሱም ድምፃቸውን ከፍ አድርገው እንደ ገና አለቀሱ፤ ከዚያም ዖርፋ አማ ቷን ስማ ተሰናበተቻት፤ ሩት ግን ልትለ ያት ስላልፈለገች ተጠመጠመችባት።

[15]ኑኃሚን መልሳ፣ “እነሆ የባልሽ ወንድም ሚስት ወደ ወገኖቿና ወደ አማልክቷ ተመል ሳለች፤ አብረሻት ተመለሽ” አለቻት።

[16]ሩት ግን እንዲህ አለች፤ “ተለይቼሽ እን ድቀር ወይም እንድመለስ አትለማመጭኝ፤ ወደምትሄጂበት እሄዳለሁ፤ በምትኖሪበትም እኖራለሁ፤ ሕዝብሽ ሕዝቤ፤ አምላክሽ አምላኪ ይሆናል። [17]በምትሞቺበት እሞታለሁ፤ እዚ ያው እቀበራለሁ። ከእንግዲህ ሞት ከሚለየን በቀር ብለይሽ *እግዚአብሔር* ይፍረድብኝ፤ ከዚህም የከፋ ያድርግብኝ።” [18]ሩት አብራት ለመሄድ መቍረጧን በተረዳች ጊዜ፣ ኑኃሚን መጐትጐቷን ተወች።

[19]ከዚያም ሁለቱ ሴቶች እስከ ቤተ ልሔም ድረስ ተጓዙ፤ ቤተ ልሔም እንደ ደረሱም፣ በእነርሱ ምክንያት ከተማው በሙሉ ተተረ ማመሰ፤ ሴቶቹም፣ “ይህች ኑኃሚን ናትን?” በማለት ተገረሙ።

[20]እርሷም እንዲህ አለች፤ “ሁሉን የሚችል አምላክ[ሀ] ሕይወቴን እጅግ መራራ አድርጎ ታልና ማራ[ለ] በሉኝ እንጂ፣ ኑኃሚን[ሐ] ብላችሁ አትጥሩኝ። [21]በሙላት ወጣሁ፤ ነገር ግን *እግዚአብሔር* ባዶዬን መለሰኝ፤ *እግዚአብሔር* አስጨንቆኛል[መ]፣ ሁሉን የሚችል አምላክ መከራ አምጥቶብኝ ሳለ እንዴት ኑኃሚን ብላችሁ ትጠሩኛላችሁ?” አለቻቸው።

[22]ስለዚህ ኑኃሚን ከምራቷ ከሞዓባዊቷ ሩት ጋር በመሆን ከሞዓብ ተመለሰች፤ ቤተ ልሔም የደረሱትም የገብስ አዝመራ በሚሰበሰብበት ወቅት መጀመሪያ ላይ ነበር።

## ሩት በቦዔዝ ዕርሻ

**2** ኑኃሚን፤ ከአቤሜሌክ ጐሣ የሆነ ቦዔዝ የሚባል ባለጸጋ የባል ዘመድ ነበራት። [2]ሞዓባዊቷ ሩትም ኑኃሚንን፣ “በፊቱ ሞገስ አግኝቼ ቃርሚያ የሚያስቃርመኝ ሰው ባገኝ

29፥11፤ዘኍ25፥6፤ ሩት3፥1
1፥11 ዘፍ38፥11፤ ዘዳ25፥5
1፥13 ቍ20፤ ዘፍ38፥11፤ዘፀ1፥14፤ 15፥ 23፤መሳ2፥15፤ 1ሳሙ30፥6፤ኢዮ4፥5
1፥14 ቍ9፤ ዘፍ31፥28፤ዘዳ10፥20፤ ሩት2፥11፤3፥11 ሚክ7፥6
1፥15 ዘዳ25፥7፤ ኢሱ24፥14
1፥16 ዘፍ24፥58፤ ኢሱ24፥15፤ 2ነገ2፥2፤መዝ45፥10
1፥17 1ሳሙ3፥17፤ 14፥44፤20፥13፤ 25፥22፤2ሳሙ3፥9፡ 35፤15፥21፤19፥13፤ 1ነገ2፥23፤19፥2፤ 20፥10፤2ነገ6፥31
1፥18 ሐሥ21፥14
1፥19 መሳ17፥7፤ ማቴ21፥10
1፥20 ቍ13፤ ዘፍ15፥1፤17፥1፤ መዝ91፥1
1፥21 ኢዮ1፥21፤ 30፥11፤መዝ88፥7፤ ኢሳ53፥4
1፥22 ዘፍ11፥31፤ ዘፀ9፥31፤ዘሌ19፥9፤ ሩት2፥2፡6፡21፤4፥5፡ 10፤2ሳሙ21፥9
2፥1 ሩት1፥2፤3፥2፤ 4፥21፤1ሳሙ9፥1፤ 1ነገ11፥28፤ 1ዜና2፥12፤ምሳ7፥4፤ ማቴ1፥5፤ሉቃ3፥32

2፥2 ዘፍ6፥8፤18፥3፤ ዘሌ19፥9፤23፥22፤ሩት1፥22

[ሀ]20 በዚህና በቍጥር 21 ላይ ዕብራይስጡ፣ *ሻዳይ* ይላል።
[ለ]20 *ማራ* ማለት *መራራ* ማለት ነው። [ሐ]20 በዚህና በቍጥር 21 ላይ፣ *ኑኃሚን* ማለት *ደስተኛ* ማለት ነው። [መ]21 ወይም *እግዚአብሔር ፈተነኝ*

1፥11 *ባል የሚሆኗችሁ ሌሎች ልጆች የምወልድ ይመስላችኋል?* ኑኃሚን እዚህ ላይ ይህን ያለችው ለመበለቶች ከለላ የሚሆነውንና የቤተ ሰብ የትውልድ ሐረግ እንዳይቋረጥ የሚያረጋግጠውን የእስራኤላውያንን ሕግ ተመርኵዛ ነው (የዘፍ 38፥8፤ ዘዳ 25፥5-10 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ማር 12፥18-23)።

1፥12 *አርጅቻለሁ፤* ኑኃሚን ከእንግዲህ ልጅ ሊኖራት አይችልም፤ ማሕፀኗም ባዶ ነው።

1፥13 *እግዚአብሔር ተቈጥቶኛልና፤* የቍ5-6፡ እና 20-21 ማብ ይመ።

*1፥14፤* የዖርፋ ተሰናብታ መሄድ፣ ሩት ለምስኪን ምራቷ ያላትን ጽኑ ታማኝነት አጒልቶ ያሳያል።

1፥15 *አማልክቷ፤* ዋናው የሞዓባውያን የጣዖት አምላክ ካሞሽ ነው (ዘኍ 21፥29 እና 1ነገ 11፥7፤ የ2ነገ 3፥26-27 ማብ ይመ)።

*1፥16፤* ታማኝነትንና ፍቅርን የሚያመለክተው ይህ ዝነኛና የቈየ አባባል፣ የሩትን እውነተኛ ባሕርይ ይገልጻል። ለኑኃሚን የነበራት ታማኝነት ፍጹም ከመሆኑ የተነሣ የኑኃሚንን ሐዘን ልትካፈል ወደደች። ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ታማኝነትን ለማየት 2ሳሙ 15፥21 ይመ።

1፥17 *ብለይሽ እግዚአብሔር ይፍረድብኝ፤* የ1ሳሙ 3፥17 ማብ ይመ። ሩት ከአሕዛብ ወገን ሆና ሳለ ለኑኃሚን ያላትን ታማኝነት ለመግለጽ በእስራኤል አምላክ ስም ማለች፤ በዚህም ዐይነት የእስራኤልን አምላክ አምላኳ አደረገች (ቍ 16 ይመ)።

1፥20 *ማራ ... ኑኃሚን፤* “ማራ” በዕብራይስጥ “መራራ” ማለት ሲሆን፣ “ኑኃሚን” ማለት ደግሞ “አስደሳች” ማለት ነው። በጥንቱ የመካከለኛው ምሥራቅ የሰዎች ስም ትርጕም አለው። *ሁሉን የሚችል፤* የዘፍ 17፥1 ማብ ይመ።

1፥21 *በሙላት ... ባዶዬን፤* እነዚህ ሁለት ቃላት የታሪኩን ጭብጥ ወይም ማእከላዊ ሐሳብ በጒልህ ያሳያሉ፤ ባዶዋን የቀረችው ኑኃሚን እንደ ገና ሙሉ ሆነች።

1፥22 *ከሞዓባዊቷ ሩት፤* ጸሓፊው፣ ሩት የባዕድ አገር ሰውና ከተናቀ ሕዝብ መካከል የመጣች ሴት መሆኗን ደጋግሞ ይገልጻል (2፥2፡6፡21፤ 4፥5፡10 እና 2፥10 ይመ)። *አዝመራ፤* በጥንታዊቷ ከነዓን አዝመራ የሚሰበሰበው በመጋቢትና በሚያዝያ ወር ነው (በመጀመሪያ የሚሰበሰበው ገብስ ሲሆን፣ ከጥቂት ሳምንት በኋላ የሚሰበሰበው ስንዴ ነበር፤ 2፥23 ይመ)። የመከሩ አሰባሰብ ሂደት ከዚህ የሚከተለውን ይመስላል፤ (1) የደረሰው ሰብል በማጭድ ይታጨዳል (ዘዳ 16፥9፤ 23፥25፤ ኤር 50፥16፤ ኢል 3፥13)፤ አብዛኛውን ጊዜ ሰብሉን የሚያጭዱት ወንዶች ናቸው፤ (2) የታጨደው ሰብል በነዶ ይታሰራል፤ አብዛኛውን ጊዜ ሰብሉን በነዶ በነዶ የሚያስሩት ሴቶች ናቸው፤ (3) ሰብሉ ሲታጨድ የተረፈው ይቃረማል (2፥7)፤ (4) በነዶ በነዶ የታሰረው ሰብል ወደ መውቂያው ዐውድማ ይወሰዳል፤ ነዶው ወደ ዐውድማ የሚወሰደው በአህያ ወይም በጋሪ ተጭኖ ነው (አሞ2፥13)፤ (5) እህሉን ወይም ፍሬውን ከገለባው ለመለየት ይበራያል፤ እህሉ የሚወቃው በከብቶች በማበራየት ሲሆን (ዘዳ25፥4፤ ሆሴ 10፥11) አንዳንድ ጊዜ ግን ጥርስ ባለው የማሄጃ ወይም የመውቂያ መሣሪያ ይወቃል (ኢሳ 41፥15፤ አሞ 1፥3) ወይም የጋሪ መንኰራኵር እንዲሄድበት ይደረጋል (ኢሳ 28፥28)፤ (6) እህሉን ለአየር በመስጠት ወይም ወደ ሰማይ በመበተን በመንሽ ይበጠራል (ኤር 15፥7)፤ እህሉ ለአየር የሚሰጠው ከቀትር በኋላ ለጥቂት ሰዓት የሚነፍሰው ነፋስ ፍሬውን ከገለባው እየለየ በአበጣሪው እግር ሥር እንዲያስቀር ነው (መዝ 1፥4)፤ (7) እህሉ ከዐሠሩ እንዲለይ ይነፋል (አሞ 9፥9)፤ (8) እህሉ በቀላሉ እንዲጓጓዝም በስልቻ ይከተታል (ዘፍ 42፥44)። የመውቂያ ዐውድማዎች የተደለደሉና የለሰለሱ ሲሆኑ፣ እህሉን ለአየር ለመስጠት እንዲያመቹ በጥንቃቄ የተመረጡ ቦታዎች ናቸው። ለዐውድማው የሚመረጡ ቦታዎች አብዛኛው ጊዜ ከመንደሩ በስተ ምሥራቅ ነው። *መጀመሪያ፤* ኑኃሚንና ሩት ቤተ ልሔም ሲደርሱ አዝመራ የሚሰበሰብበት ወቅት ገና መጀመሩ ነበር፤ ይህም ባዶዋን የቀረችው ኑኃሚን ሙሉ እንደምትሆን አስቀድሞ የሚያመለክት ነው። የገብስ መከር የሚሰበሰብበት ወቅት ስለመድረሱ የተሰጠው መግለጫ በመከር መሰብሰቢያው ዕርሻ ላይ ወደፊት የሚታየው ትዕይንት ምን እንደሚመስል እንዲገነዘብ አንባቢውን አስቀድሞ ያዘጋጃል (በመግቢያው ላይ “ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ” የሚለውን ይመ)።

2፥1 *ቦዔዝ፤* በዕብራይስጥ ምናልባት “በእርሱ ኀይል አለ” የሚል ትርጓሜ አለው፤ ቦዔዝ በሁለቱም የኢየሱስ የትውልድ ሐረጎች ውስጥ ስሙ ተጠቅሶአል (ማቴ 1፥5፤ ሉቃ 3፥32)። *ዘመድ፤* ለኑኃሚን የተስፋ ምልክት ነው (የቍ 20 ማብ ይመ)።

2፥2 *እሰቲ ... ልሂድ፤* ሩት ምንም እንኳ መጻተኛና

እስቲ ወደ እህል አዝመራው ልሂድ" አለቻት::

ኑኃሚንም፣ "ልጄ ሆይ፤ ይሁን ሂጂ" አለቻት:: [3]ስለዚህ እርሷም ወጣች፤ ከዐጫጆች ኋላ ኋላ እየተከታተለችም ከአዝመራው ቦታ ትቃርም ጀመር፤ እንዳጋጣሚ ትቃርምበት የነበረው አዝመራ ከአቤሜሌክ ጐሣ የሆነው የቦዔዝ ነበር::

[4]በዚሁ ጊዜ ቦዔዝ ከቤተ ልሔም መጣ፤ ዐጫጆቹንም፣ "እግዚአብሔር ከእናንተ ጋር ይሁን" ብሎ ሰላምታ ሰጣቸው::

እነርሱም፣ "እግዚአብሔር ይባርክህ" ብለው መለሱለት::

[5]ከዚያም ቦዔዝ የዐጫጆቹን አለቃ፣ "ይህች ወጣት ሴት የማን ናት?" ሲል ጠየቀው::

[6]የዐጫጆቹም አለቃ እንዲህ ሲል መለሰ፤ "ከኑኃሚን ጋር ከሞዓብ ምድር ተመልሳ የመጣች ሞዓባዊት ናት:: [7]እርሷም፣ 'ዐጫጆቹን እየተከተልሁ በነዶው መካከል እንድ ቃርም እባክህ ፍቀድልኝ' አለችኝ:: ለጥቂት ጊዜ በመጠለያው ከማረፏ በስተቀር ወደ አዝመራው ቦታ ገብታ ከጥዋት አንሥቶ እስካሁን ያለማቋረጥ ስትቃርም ቈይታለች::"

[8]ስለዚህም ቦዔዝ ሩትን፣ "ልጄ ሆይ ስሚኝ፤ ከእንግዲህ ወደ ሌላ አዝመራ ሄደሽ አትቃርሚ፤ ከዚህም አትራቂ፤ ከሴቶች ልጆቼ ጋር እዚሁ ሁኚ:: [9]ወንዶቹ የሚያጭዱበትን ዕርሻ ልብ እያልሽ ልጃገረዶቹን ተከተዪ፤ ወንዶቹ እንዳያስቸግሩሽም አስጠንቅቄአቸዋለሁ፤ ውሃ ሲጠማሽ ደግሞ እየሄድሽ ወንዶቹ ሞልተው ካስቀመጡት እንስራ ቀድተሽ ጠጪ::"

[10]በዚህ ጊዜ ወደ መሬት ዝቅ ብላ እጅ ነሣችው:: እርሷም፣ "ባይተዋር የሆንሁትን እኔን ታስበኝ ዘንድ በፊትህ ሞገስ ለማግኘት የበቃሁት እንዴት ነው?" አለችው::

[11]ቦዔዝም መልሶ እንዲህ አላት፤ "ባልሽ ከሞተ ጀምሮ ለዐማትሽ ያደረግሽላትን ሁሉ፣ አባት እናትሽን እንዲሁም የተወለድሽበትን አገር ትተሽ ቀድሞ ከማታውቂው ሕዝብ ጋር ለመኖር እንዴት እንደመጣሽ ነግረውኛል:: [12]ስላደረግሽው ሁሉ እግዚአብሔር ዋጋሽን ይክፈልሽ፤ በክንፉ ጥላ ሥር ለመጠለል የመጣሽበት የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር ብድራትሽን አትረፍርፎ ይመልስልሽ::

[13]እርሷም መልሳ፣ "ጌታዬ ሆይ፤ ምንም እንኳ ከሴት ሠራተኞችህ እንደ አንዲቱ መቈጠር የማይገባኝ ብሆንም እንድጽናና አድርገኸኛል፤ እንዲሁም እኔን አገልጋይህን በመልካም ንግግር ደስ አሰኝተኸኛል፤ ስለዚህ ሞገስህ እንዳይለየኝ እለምንሃለሁ" አለችው::

[14]በምሳ ሰዓት ቦዔዝ፣ "ወደዚህ ቀረብ በዪ፤ እንጀራም ወስደሽ በወይን ሆምጣጤው አጥቅሺ" አላት::

እርሷም ከዐጫጆች አጠገብ እንደ ተቀመጠች ቦዔዝ የተጠበሰ እሸት ሰጣት፤ የቻለችውንም ያህል በልታ ጥቂት ተረፋት:: [15]ለመቃረም ስትነሣም፣ ቦዔዝ ጐበዛዝቱን እንዲህ ብሎ አዘዛቸው፤ "በነዶው መካከል እንኳ ብትቃርም ክፉ አትናገሯት፤ [16]ይልቁንም ከየታሰረው ነዶ ላይ ጥቂት ጥቂቱን ዘለላ እየመዘዛችሁ በመጣል እንድታነሣው ተዉላት፤ አታስቀይሟት::"

[17]ስለዚህ ሩት እስኪመሽ ድረስ ከአዝመራው ላይ ቃረመች፤ ከዚያም የሰበሰበችውን ገብስ ወቃች፤ አንድ የኢፍ መስፈሪያም[a] ያህል ሆነ:: [18]ያንንም ይዛ ወደ ከተማ ሄደች፤ አማቷም የሰበሰበችው ምን ያህል እንደ ሆነም አየች፤ እንዲሁም ሩት የሚበቃትን ያህል ከበላች በኋላ አስተርፋ የነበረውን አውጥታ ለእርሷ ሰጠቻት::

[19]አማቷም፣ "ዛሬ የቃረምሽው ከየት ነው? የትስ ቦታ ስትሠሪ ዋልሽ? መልካም ነገር ያደረገልሽ ሰው የተባረከ ይሁን" አለቻት::

ከዚያም ሩት ስትሠራ ስለዋለችበት ስፍራ ባለቤት ለአማቷ ነገረቻት፤ እርሷም፣ "ዛሬ ስቃርም የዋልሁበት አዝመራ ባለቤት ስሙ ቦዔዝ ይባላል" አለቻት::

[20]ኑኃሚንም ምራቷን፣ "በጎነቱን ለሕያዋንም ሆነ ለሙታን ማድረጉን ያልተወ እግዚአብሔር ይባርከው" አለቻት፤ ቀጥላም፣ "ሰውየው እኮ የሥጋ ዘመዳችን ነው፤ የመቤዠት ግዴታ ካለባቸው ዘመዶቻችን አንዱ እርሱ ነው" አለቻት::

[a]17 22 ሊትር ያህል ነው::

2፥3 ቀኁ1:14፤ 2ነገ4፥18፤ኤር9፥22፤ አሞ9፥13
2፥4 ዘፍ28፥3፤ ዘኍ6፥24፤መሳ6፥12፤ ሉቃ1፥28፤2ተሰ3፥16
2፥6 ሩት1፥22
2፥7 ዘፍ37፥7፤ ዘሌ19፥9፤2ሳሙ4፥5
2፥10 ቀኁ19፤ ዘፍ19፥1፤31፥15፤ ዘዳ15፥3፤1ሳሙ20፥41
2፥11 ሩት1፥5:14: 16-17፤ኢሳ55፥5
2፥12 ኢሱ24፥15፤ 1ሳሙ24፥19፤ 26፥23:25፤ መዝ17፥8፤18፥20፤ 36፥7፤57፥1፤61፥4፤ 63፥7፤71፥1፤91፥4፤ ምሳ25፥22፤ኤር31፥16
2፥13 ዘፍ18፥3
2፥14 ቀኁ3:18፤ ዘፍ3፥19፤ዘሌ23፥14
2፥15 ዘፍ37፥7፤ ዘሌ19፥9
2፥16 ዘፍ37፥10
2፥17 ዘሌ19፥36፤ መሳ6፥11
2፥18 ቀኁ14
2፥19 ቀኁ10
2፥20 ዘፍ11፥31፤ 19፥19፤ዘሌ25፥25፤ መሳ17፥2፤ሩት3፥9: 12፤4፥1:14፤ 1ሳሙ23፥21

ብቸኛ ወጣት ሴት ብትሆንም፣ በዕርሻ ቦታ ሊያጋጥም የሚችለውን መደፈር ሳትፈራ ለአማቷ የሚያስፈልገውን እህል ልትቃርም ሄደች:: በ3፥1 ላይ ኑኃሚን ለሩት የሚያስፈልገውን ልታዘጋጅ ተነሣች:: *ቃርሚያ እንድትቃርም፤* የዕርሻ ባለቤቶች መከር በሚሰበሰብበት ወቅት የሚወዳድቀውን ቃርሚያ ድኾች፣ መጻተኞች፣ መበለቶችና አባት የሌላቸው ልጆች የሚያስፈልጋቸውን መሰብሰብ እንዲችሉ በዚያው እንዲተውት የሙሴ ሕግ ያዛል (ዘሌ 19፥9፤ 23፥22፤ ዘዳ 24፥19)::

2፥3 *እንዳጋጣሚ፤* እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሚያስፈልገውን ያዘጋጅ ነበር (ቀኍ 19፥20)::

*2፥4፤* ቦዔዝና ዐጫጆቹ የተለዋወጡት ሰላምታ፣ ቦዔዝ የእግዚአብሔር ሰውና ቸር መሆኑን ያመለክታል::

2፥9 *ልጃገረዶቹን ተከተዪ፤* ወንዶች የደረሰውን እህል ሲያጭዱ፣ ሴቶች ደግሞ ከሥር ከሥር እየተከተሉ እህሉን በነዶ በነዶ ማሰር የተለመደ ነው፤ ስለዚህ ሩት የወዳደቀውን እህል መቃረም ችላ ነበር (የ1፥22 ማብ ይመ)::

*2፥11፤* ሩት በኀዘን የተኮማተረችውን አማቷን ለመንከባከብ ያሳየችው ታማኝነት የመጽሐፉ መሪ ሐሳብ ነው::

2፥12 *በክንፉ ጥላ፤* ወፍ ጫጩቶቿን ከክንፎቿ በታች አድርጋ እንደምትንከባከብ የሚያሳይ ምሳሌ ነው (ማቴ 23፥37፤ እንዲሁም የ3፥9 ማብ ይመ)::

2፥13 *እኔን አገልጋይህን፤* የሩትን ትሕትና የሚያሳይ አነጋገር ነው::

2፥15 *ጐበዛዝቱን፤* ቦዔዝ ሕጉ ከሚፈቅደው በላይ በመሄድ ሩት የቻለችውን ያህል መቃረም እንድትችል ፈቀደላት (3፥15 ይመ)::

2፥17 *ወቃች፤* የ1፥22 ማብ ይመ:: እንደ ጌዴዎን ሁሉ (መሳ 6፥11) የሩትም እህል ጥቂት በመሆኑ እህሉ የተወቃው በዱላ ወይም በበትር ነው::

2፥20 *በጎነቱን ... ማድረጉን ያልተወ እግዚአብሔር፤* 1፥8 ይመ፤ በ3፥10 ላይ ቦዔዝ ለሩት ያለውን ምኞች በተመሳሳይ ሁኔታ ገልጾአል:: *የመቤዠት ግዴታ ካለባቸውም ዘመዶቻችን አንዱ እርሱ ነው፤* በመጽሐፈ ሩት ውስጥ መቤዠት የሚለው ቍልፍ ነው (በመግቢያው ላይ "መሪ ሐሳቡና ትምህርተ መለኮቱ"

[21]ከዚያም ሞዓባዊቷ ሩት፣ "ደግሞም፣ 'እህሉን ሁሉ ዐጭደው እስኪጨርሱ ድረስ ከሠራተኞቼ አትለዪ! ብሎኛል" አለቻት። [22]ኑኃሚንም ምራቷን ሩትን፣ "የኔ ልጅ፤ እንዲህ ካልሽማ ከሴት ሠራተኞቹ ጋር አብሮ መሄድ ይሻልሻል፤ ወደ ሌላ ሰው አዝመራ ብትሄጂ ጉዳት ሊያገኝሽ ይችላልና" አለቻት። [23]ስለዚህ የገብሱና የስንዴው አዝመራ ተሰብስቦ እስኪያበቃ ድረስ ሩት የቦዔዝን ሴቶች ሠራተኞች ተጠግታ ቃረመች፤ ከአማቷም ጋር ኖረች።

## በዔዝና ሩት በእህል ዐውድማው ላይ

**3** ከዚህ በኋላ አማቷ ኑኃሚን፣ ሩትን እን ዲህ አለቻት፤ "ልጄ ሆይ፤ የሚመችሽን ቤት[a] እንድፈልግልሽ አይገባኝምን? [2]ከሴቶች ሠራተኞቹ ጋር አብረሽ የነበርሽበት በዔዝ ዘመዳችን አይደለምን? ዛሬ ማታ በዐውድማው ላይ ገብስ ያበራያል፤ [3]ተጣጠቢ፤ ሽቶ ተቀቢ፤ እንዲሁም የክት ልብስሽን ልበሺ፤ ከዚያም ወደ ዐውድማው ውረጂ፤ ይሁን እንጂ በልቶና ጠጥቶ እስኪያበቃ ድረስ እዚያ መሆንሽን እንዳያውቅ ይሁን። [4]በተኛም ጊዜ፣ የሚተኛበትን ቦታ ልብ ብለሽ እዩና ሄደሽ እግሩን ገልጠሽ ተኚ፤ ከዚያም የምታደርጊውን ራሱ ይነግርሻል።"

[5]ሩትም፣ "ያልሽውን ሁሉ አደርጋለሁ" አለቻት። [6]ስለዚህ ተነሥታ ወደ ዐውድማው ወረደች፤ አማቷ አድርጊ ያለቻትንም ሁሉ አደረገች።

[7]በዔዝ በልቶ ጠጥቶ ከጨረሰና ደስም ከተሰኘ በኋላ፣ ራቅ ካለው የእህል ክምር አጠገብ ለመተኛት ሄደ። ሩት በቀስታ ከአጠገቡ ደረሰች፤ እግሩንም ገልጣ ተኛች። [8]እኩለ ሌሊት ላይ ሰውዬውን አንዳች ነገር አስደነገጠው፤ ገልበጥ ሲልም አንዲት ሴት እግርጌው ተኝታ አገኘ።

[9]እርሱም፣ "አንቺ ማነሽ?" ሲል ጠየቀ።

እርሷም፣ "እኔ አገልጋይህ ሩት ነኝ፤ መቤዠት የሚገባህ ቅርብ የሥጋ ዘመድ አንተ ነህና ልብስህን ጣል አድርግብኝ" አለችው።

[10]እርሱም መልሶ እንዲህ አላት፤ "ልጄ ሆይ፤ እግዚአብሔር ይባርክሽ፤ ከዚህ በፊት ካደረግሽው ይልቅ ያሁኑ በጎነትሽ ይበልጣል፤ ባለጠጋም ሆነ ድኻ ወጣት ወንድ ፈልገሽ አልሄድሽምና። [11]አሁንም ልጄ ሆይ፤ አትፍሪ፤ የምትጠይቂውን ሁሉ አደርግልሻለሁ፤ አንቺ ምግባረ መልካም ሴት መሆንሽንም የአገሬ ሰው ሁሉ ያውቀዋል። [12]ምንም እንኳ እኔ ቅርብ የሥጋ ዘመድ መሆኔ የተረጋገጠ ቢሆንም፣ ከእኔ ይልቅ መቤዠት የሚገባው ቅርብ የሥጋ ዘመድ አለ። [13]ዛሬ ሌሊቱን እዚሁ ዕደሪ፤ ሲነጋም ሰውየው ሊቤዥሽ ከፈለገ፣ መልካም ነው ይቤዥሽ፤ የማይፈልግ ከሆነ ግን በሕያው እግዚአብሔር እምላለሁ፤ እኔ እቤዥሻለሁ፤ እስኪነጋም ድረስ እዚሁ ተኚ።"

[14]ስለዚህም ሩት እስኪነጋ ድረስ እግርጌው ተኛች፤ ዳሩ ግን ማንም ሰው ተለይቶ ሊታወቅ በማይችልበት ሰዓት ቀደም ብላ ተነሣች፤ እርሱም፣ "ሴት ወደዚህ ዐውድማ መምጣቷ እንዳይታወቅ" አላት።

[15]እንዲሁም፣ "በላይሽ የደረብሽውን ልብስ አቅርቢልኝ፤ ዘርግተሽም ያዢው" አላት፤ ዘርግታ እንደ ያዘችም፤ ስድስት መስፈሪያ ገብስ ሰፍሮ አሸከማት፤ ከዚያም ወደ ከተማ ተመለሰች[b]።

2፥21 ሩት1፥22
2፥23 ዘፍ30፥14፤ ዘፀ9፥31፤1ሳሙ6፥13
3፥1 ሩት1፥9፡14
3፥2 ዘሌ2፥14፤ ዘኁ18፥27፤ መሳ6፥11፤ሩት2፥1
3፥3 ዘፍ41፥14፤ ዘፀ32፥6፤ 2ሳሙ12፥20፤14፥2፤ 2ነገ5፥10፤መዝ26፥6፤ 51፥2፤መክ2፥3፤ ኢሳ1፥16፤61፥3፤ ኤር4፥14፤15፥17፤ ሕዝ16፥9
3፥5 ኤፌ6፥1፤ ቈላ3፥20
3፥6 ዘኁ18፥27
3፥7 መሳ19፥6፡22፤ 1ሳሙ25፥36፤ 2ሳሙ13፥28፤ 1ነገ21፥7፤2ዜና31፥6፤ አስ1፥10፤ ማሕ7፥2፤ኤር5፥26፤ ሐጌ2፥16
3፥9 ሩት2፥20፤ ሕዝ16፥8
3፥10 ኢሱ2፥12፤ መሳ17፥2
3፥11 ምሳ12፥4፤ 14፥1፤31፥10
3፥12 ሩት2፥20፤ 4፥1
3፥13 ዘኁ14፥21፤ ዘዳ25፥5፤ሩት4፥5፡6፤ ሆሴ4፥15፤ ማቴ22፥24
3፥14 ዘኁ18፥27፤ ሮሜ14፥16፤ 2ቆሮ8፥21
3፥15 ኢሳ3፥22

[a]1 ወይም *የምታርፍበትን*
[b]15 አንዳንድ የዕብራይስጥ ቅጆች ግን *ተመለሰ* ይላሉ።

የሚለውን ይመ)። የቅርብ ዘመድ የሆነና የመቤዠት ኀላፊነት ያለበት ሰው በቤተሰቡም ሆነ በቤተ ዘመዱ ውስጥ ለሚገኙት ምስኪኖች ክብካቤ የማድረግ ኀላፊነት አለበት፤ ለምሳሌ በሞት ለተለየው ወንድሙ ወራሽ መተካት (ዘዳ 25፥5-10)፣ በችግር ምክንያት መሬቱን ከቤተ ሰቡ ውጭ የሸጠውን የዘመዱን መሬት መዋጀት (ዘሌ 25፥25-28)፣ በድኽነት ምክንያት ለባርነት የተሸጠውን ዘመዱን መቤዠትና (ዘሌ 25፥47-49) የሟች ዘመዱን ደም መበቀል ይኖርበታል (ዘኍ 35፥19-21፤ "መበቀል" የሚለውና "መቤዠት" የሚሉት ቃላት የተተረጐሙት ከአንድ የዕብራይስጥ ቃል ነው)። ኑኃሚን እግዚአብሔር ሩትን ሊቤዣት ወደሚችል ወደ ዘመዷ እርሻ እንደመራት ስትሰማ ተጽናናች፤ ይህ የኑኃሚንን ተስፋ ያለመለመው መለኮታዊ ምሪት በታሪኩ ውስጥ ወሳኝ ቦታ አለው።

2፥23 *የገብሱና የስንዴው አዝመራ ተሰብስቦ እስኪያበቃ፤* ይህ ሐረግ መከር በሚሰበሰብበት ወቅት የተፈጸመውን ድርጊት ደምድሞ በመውቂያው ዐውድማ ላይ ወደሚካሄደው ትዕይንት ያሸጋግራል።

*3፥1* ኑኃሚን ተስፋዋ በመለምለሙ (ከ1፥8-13 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ስለ ሩት የወደፊት ኑሮ ማሰብ ጀመረች (የ2፥2 ማብ ይመ)።

3፥2 *ዛሬ ማታ ... ገብስ ያበራያል፤* የ1፥22 ማብ ይመ። እህል በሚወቃበት ወቅት የመሬቱ ባለቤት እህሉን ከሌቦች ለመጠበቅ በዐውድማው አካባቢ ማደሩ የተለመደ ነበር።

*3፥3* ሩት ራሷን እንደ ሙሽራ እንድታዘጋጅ መመሪያ ተሰጣት (ሕዝ 16፥9-12 ይመ)። *ወደ ዐውድማው ውረጂ፤* እህል ወቂዎች ወደ አመሻሹ ላይ እየዘፈኑ በሚጨፍሩበት ቦታ ሴቶች አይገኙም (ቍ 14)። *በልቶና ጠጥቶ፤* የመከር ጊዜ የደስታና የፈንጠዝያ ጊዜ ነው (ኢሳ 9፥3፤ 16፥9-10፤ ኤር 48፥33)።

3፥4 *እግሩን ገልጠሽ ተኚ፤* ኑኃሚን ለሩት የሰጠቻት ምክር የማቻኩል መስሎ ቢታይም እንኳ፣ የኑኃሚንና የሩት ታማኝነት ግን የሚያጠያይቅ አይደለም፤ (ቍ11 ይመ)። ኑኃሚን ለሩት የሰጠቻት ምክር፣ በዔዝ የመቤዠት ኀላፊነቱን እንዴት እንደሚወጣ የሚያነሣሣ ነው። ሩት የፈጸመችው ድርጊት የጋብቻ ጥያቄ ነው። የፋሬስ እናት ትዕማር የመቤዠትን ሕግ ከለላዋ ስታደርግ ይታያል (4፥12፤ ዘፍ 38፥13-30 ይመ)።

3፥9 *ልብስህን ጣል አድርግብኝ፤* ይህ የጋብቻ ጥያቄ ነው (ሕዝ16፥8 ይመ)፤ በአሁኑም ጊዜ ቢሆን በአንዳንድ የመካከለኛው ምሥራቅ አገሮች ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ነገር ሲፈጸም ይታያል።

3፥10 *ከዚህ በፊት ካደረግሽው ይልቅ... በጎነትሽ፤* 2፥11-12 ይመ።

3፥11 *ምግባረ መልካም ሴት፤* ምሳ 31፥10 ይመ። በዚህ ቍጥር ላይ የምናገኘው የዕብራይስጡ አገላለጽ በዔዝ በ2፥1 ላይ ከተናገረው ጋር ተመሳሳይ ነው፤ ይህም ጸሐፊው ለሩትና ለበዔዝ ያለው ግምት እኩል መሆኑን ያሳያል።

3፥12 *ከእኔ ይልቅ መቤዠት የሚገባው ቅርብ የሥጋ ዘመድ አለ፤* በዔዝ ከቀድሞው የሩት ባል (መሐሎን) ጋር ያለው ዝምድና ምን እንደሆነ አይታወቅም፤ ይሁን እንጂ የመበለቲቱ የቅርብ ዘመድ እርሷን የማግባት ግዴታ አለበት። ሩት በዔዝን እንድትቀርብ ኑኃሚን ምክር የሰጠችው፣ በዔዝ ለሩት ከለላዋ ለመሆን ፈቃደኛ በመሆኑ ነው። በዔዝ ግን ዋርሳ መሆን ያለበት የቅርብ ዘመዱ እንደሆነ በሕግ የተጻፈውን ችላ ሊል አልፈለገም።

3፥13 *በሕያው እግዚአብሔር እምላለሁ፤* በዔዝ የቤተ ሰቡን ንብረት ለመዋጀትና ሩትን ለማግባት ቃለ መሐላ ፈጸመ (ከ1፥17 ጋር ያነጻጽሩ)።

*3፥15፤* በዔዝ ሕጉ ከሚፈቅደው በላይ በመሄድ ለሩት ከአውድማው ላይ ብዙ እህል ሰፈረላት (2፥15 ይመ)።

[16]ሩት ወደ አማቷ እንደ ተመለሰች፣ ኑኃሚን፣ "ልጄ ሆይ፤ የሄድሽበት ጉዳይ እንዴት ሆነ?" ብላ ጠየቀቻት።

ሩትም ቦዔዝ ያደረገላትን ሁሉ ነገረቻት፤ [17]ቀጥላም፣ " 'ወደ አማትሽ ባዶ እጅሽን አትመለሺ' በማለት ይህን ስድስት መስፈሪያ ገብስ ሰጠኝ" አለቻት።

[18]ኑኃሚንም፣ "ልጄ ሆይ፤ የሚሆነውን ነገር እስክታውቂ ድረስ ታገሺ፤ ጉዳዩ ዛሬውኑ እልባት ካላገኘ ሰውየው አያርፍም" አለቻት።

## ቦዔዝ ሩትን አገባ

**4** ቦዔዝም ወደ ከተማዪቱ በር አደባባይ ወጥቶ ተቀመጠ፤ እርሱም የመቤዠት ቅድሚያ ያለው የቅርብ ዘመድ በመጣ ጊዜ፣ "ወዳጄ ሆይ፤ ወደዚህ ና፤ እጠገቤም ተቀመጥ" አለው፤ ስለዚህም ሰውየው ሄዶ ተቀመጠ።

[2]ቦዔዝ ከከተማዪቱ ሽማግሌዎች ዐሥሩን ጠርቶ፣ "እዚህ ተቀመጡ" አላቸው፤ እነርሱም ተቀመጡ። [3]ከዚያም የመቤዠት ቅድሚያ ያለውን ቅርብ የሥጋ ዘመድ እንዲህ አለው፤ "ከሞዓብ የተመለሰችው ኑኃሚን፣ የወንድማችንን የአቤሜሌክን ጢንጦ መሬት ልትሸጥ ነው። [4]አንተም ይህንኑ ጉዳይ ማወቅ አለብህ ብዬ ስላሰብሁ፣ አሁን እዚህ በተቀመጡትና በሕዝቤም ሽማግሌዎች ፊት እንድትገዛው ላሳስብህ ወደድሁ፤ አሁንም ራስህ የምትቤዠው ከሆነ ልትቤዠው ትችላለህ፤ ለዚህ ከአንተ ቅድሚያ የሚኖረው የለም፤ ይህን የማታደርግ ከሆነ ግን ከአንተ ቀጥሎ የሚገባኝ ስለሆንሁ ንገረኝና ልወቀው።" ሰውየውም "እኔ እቤዠዋለሁ" አለ።

[5]ከዚያም ቦዔዝ፣ "እንግዲህ መሬቱን ከኑኃሚንና ከሞዓባዊቷ ከሩት ላይ በምትገዛበት ዕለት የሟቹን ስም በርስቱ ላይ ለማስጠራት ሚስቱንም አብረህ መውሰድ አለብህ" አለው።

[6]ያም ቅርብ የሥጋ ዘመድ፣ "እንዲህ ከሆንማ የራሴን ርስት አደጋ ላይ ልጥል ስለምችል እኔ ልቤዠው አልችልም፤ አንተው ራስህ ተቤዠው" አለው።

[7]በጥንት ዘመን በእስራኤል የመቤዠትም ሆነ ንብረት የማስተላለፍ ጉዳይ የሚጸናው አንዱ ወገን ጫማውን አውልቆ ለሌላው ወገን ሲሰጠው ነው፤ በእስራኤል ዘንድ መሸጥም ሆነ መግዛት ሕጋዊነት የሚኖረው በዚህ ሁኔታ ነበር።

[8]ቅድሚያ ያለው ቅርብ የሥጋ ዘመድም ቦዔዝን፣ "እንግዲህ አንተው ራስህ ግዛው" ብሎ ጫማውን አወለቀ።

[9]ቦዔዝም ለሽማግሌዎቹና ለሕዝቡ ሁሉ እንዲህ አለ፤ "የአቤሜሌክን፣ የኬሌዎንንና የመሐሎንን ንብረት በሙሉ ከኑኃሚን ላይ ለመግዛቴ በዛሬው ዕለት እናንተ ምስክሮች ናችሁ፤ [10]እንዲሁም የሟቹ ስም ከወንድሞቹ መካከልና ከአገሩ ደጅ እንዳይጠፋ፣ የሟቹን ስም በርስቱ ላይ ለማስጠራት የመሐሎን ሚስት የነበረችው ሞዓባዊት ሩትን አግብቼአታለሁ፤ እናንተም ዛሬ ምስክሮች ናችሁ።"

[11]ከዚያም ሽማግሌዎቹና በከተማዪቱ በር አደባባይ የነበሩት ሁሉ እንዲህ አሉ፤ "እኛ ምስክሮች ነን፤ እግዚአብሔር ይህችን ወደ ቤትህ የምትገባውን ሴት፣ የእስራኤልን ቤት በአንድነት እንደሠሩ እንደ ራሔልና እንደ ልያ ያድርጋት፤ አንተም በኤፍራታ የበረታህ ሁን፤ ስምህም በቤተ ልሔም የተጠራ ይሁን።

3፥18 መዝ37፥3-5
4፥1 ዘፍ18፥1፤ 23፥10፤ሩት2፥20፤ 3፥12
4፥2 ዘፀ3፥16፤ ዘዳ25፥7
4፥3 ዘሌ25፥25፤ ሩት1፥2
4፥4 ዘሌ25፥25፤ ኤር32፥7-8
4፥5 ዘፍ38፥8፤ ሩት1፥22፤3፥13
4፥6 ዘሌ25፥25፤ ዘዳ25፥7፤ሩት3፥13
4፥7 ቍ-8፤ ዘሌ25፥24፤ ዘዳ25፥7-9፤ ኢሳ8፥1-2፤16፤20
4፥8 ዘዳ25፥9
4፥9 ኢሳ8፥2፤ ኤር32፥10፤44
4፥10 ዘዳ25፥5፤6፤ ኢሱ24፥22፤ ሩት1፥22
4፥11 ዘፍ4፥19፤

---

3፥17 *ባዶ እጅሽን፤* ባዶ እጅ መቅረትና መሙላት የመጽሐፉ መሪ ሐሳብ ነው (የ1፥2 ማብ ይመ)።

3፥18 *ታገሺ፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በ4፥1 ላይ "ተቀመጠ" ተብሎ ተተርጕሞአል። በዚህ ዐይነት ጸሓፊው፣ ቦዔዝ በከተማዪቱ መግቢያ በር ላይ ተቀምጦ ሁኔ ታውን በርጋታ ሲመረምር የሚያሳየውን ዐቢይ ትዕይንት ለአንባቢ ያስተዋውቃል።

4፥1 *ወደ ከተማዪቱ በር፤* የከተማ በር በዚያን ዘመን ለነበሩት እስራኤላውያን እንደ መሰብሰቢያ አዳራሽ የሚቈጠር ሲሆን የንግድ ልውውጥና ችሎት የሚያስችሉበት ቦታ ነበር፤ በፍርድ ጊዜ ምስክሮችን በቀላሉ ማግኘት የሚቻለውም በዚህ ቦታ ነበር (ቍ 9-12፤ የዘፍ 19፥1 ማብ ይመ)። *ወዳጄ ሆይ፤* ሌላው የሥጋ ዘመድ ስሙ አልተጠቀሰም።

4፥2 *ከከተማዪቱ ሽማግሌዎች ዐሥሩን ጠርቶ፤* ፍርድና ብይን ለመስጠት በቂ ቍጥር ነው።

4፥3 *ጢንጦ መሬት ልትሸጥ ነው፤* የ2፥20 ማብ ይመ። ይህ ሐረግ ሁለት ትርጕም ሊኖረው ይችላል፤ (1) መሬቱ የኑኃሚን ሲሆን፣ ካለባት ከባድ ችግር የተነሣ ለመሸጥ ተገደደች። ከችግር የተነሣ መሬታቸውን ለመሸጥ የሚገደዱ ሰዎች ካሉ የቅርብ ዘመዳቸው መሬቱ ከቤተ ሰቡ እጅ እንዳይወጣ መግዛት አለበት። (2) መሬቱ የኑኃሚን አይደለም፤ ቤተ ሰቡ ወደ ሞዓብ ከመሄዱ በፊት አቤሜሌክ መሬቱን ሸጦታል፤ ነገር ግን በሕጉ መሠረት መሬቱን መልሳ የመግዛት መብት እንዳላት ታውቃለች። ነገር ግን መሬቱን የመግዛት ዐቅም ስለሌላት የቅርብ ዘመዷ መሬቱን እንዲገዛላት ፈለገች።

4፥5 *የሟቹን ስም በርስቱ ለማስጠራት ሚስቱንም አብረህ መውሰድ አለብህ፤* አሁን ቦዔዝ ቀሪውን ግዴታ አስታወቀ፤ ያም ግዴታ ሩትን መውሰዱ ነበር። በሙሴ ሕግ መሠረት (ዘዳ 25፥5-6) የሩት የበኵር ልጅ የመሐሎንን ስም የማስጠራትና የቤተ ሰቡን ርስት የመውረስ መብት አለው።

4፥6 *ልቤዠው አልችልም፤* መሬቱን ሊዋጅ ያልፈለገው ከሩት ልጅ ከወለደና ወራሽም ይህ ልጅ ብቻ ከሆነ፣ ያለኝ ሀብት በሙሉ ለአቤሜሌክ ቤተ ሰብ ይተላለፋል የሚል ፍራቻ ስላለው ነው (የዘፍ 38፥9 ማብ ይመ)። ይህ ሰው የወሰደው እርምጃ ቦዔዝ ከወሰደው እርምጃ በምንም አይተናነስም። ይህ የቅርብ ዘመድ የሚጠበቅበትን የመቤዠት ኀላፊነት ለመወጣት ፈቃደኛ አለመሆኑ፣ የቦዔዝን በጎነትና ቸርነት አጕልቶ ያሳያል፤ ይህም የያርፋ ወደ ቤተ ሰቦቿ መመለስ ሩት ለኑኃሚን ያላትን ጽኑ ታማኝነት አጕልቶ እንደሚያሳየው ማለት ነው።

4፥7 *አንዱ ወገን ጫማውን አውልቆ፤* አንድ ሰው ንብረቱን ለሌላ ሰው መስጠቱንና ማስተላለፉን የሚያረጋግጠው ጫማውን አውልቆ ለሰውየው በመስጠት ነው (ከአሞ 2፥6፤8፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። የኑዚ መዛግብት ከዚህ ጋር ተመሳሳይነት ያለውን ልማድ ጽፈዋል (በሁለተኛው ሺህ ምእተ ዓ ቅ ክ አጋማሽ ላይ የተጻፈ ከባቢሉይ ኪዳን ጋር የሚዛመድ ጥንታዊ ጽሑፍ ነው)።

4፥9 *ምስክሮች፤* በአደባባይ የሚመሰክሩ ሰዎች ተግባር በመግቢያ በሮች ላይ የተሰጠው ፍርድ ትክክል መሆኑንና አለመሆኑን ማረጋገጥ ነው።

4፥10 *የሟቹ ስም፤* ዘዳ 25፥6 ይመ።

4፥11 *የእስራኤልን ቤት ... እንደ ሠሩ እንደ ራሔልና እንደ ልያ፤* ከዘዳ 25፥9 ጋር ያነጻጽሩ። የሩትን መጽሐፍ የሚያነቡ እስራኤላውያን በራሔልና በልያ የተሠራው የያዕቆብ (የእስራ ኤል) ቤት ሊጠፋ በተቃረበ ጊዜ፣ የሩትና የቦዔዝ ልጅ የሆነው ዳዊት እንደ ገና ከሠራው የእስራኤል ቤት ጋር ሊያገናዝቡት ይችላሉ (1ሳሙ 4)። ከዚህ በተጨማሪ እግዚአብሔር የዳዊትን ቤት ለመሥራትና ሥርወ መንግሥቱን ለማጽናት በዚህም በኩል የተባረከው የእስራኤል ዕድል ፈንታ ይረጋገጣል (2ሳሙ 7፥27-

[12]*እግዚአብሔር* ከዚህች ወጣት ሴት በሚሰጥህ ዘር አማካይነት ቤተ ሰብ ህን ትዕማር ለይሁዳ እንደ ወለደችው እንደ ፋሬስ ቤተ ሰብ ያድርገው።"

## የዳዊት የትውልድ ሐረግ

4፥18 ተጓ ምብ - 1ዜና 2፥5-15፤ ማቴ 1፥3- 6፤ ሉቃ 3፥31- 33

[13]ስለዚህ ቦዔዝ ሩትን ወሰዳት፤ ሚስቱም ሆነች። ከዚያም ወደ እርሷ ገባ፤ *እግዚ አብሔር* እንድትፀንስ አደረጋት፤ ወንድ ልጅም ወለደች። [14]ሴቶቹም ኑኃሚንን እንዲህ አሏት፤ "ዛሬ የሚቤዥ ቅርብ የሥጋ ዘመድ ያላሳጣሽ *እግዚአብሔር* ይባረክ፤ በመላው እስራኤልም ስሙ ይግነን። [15]ልጁ ሕይወትሽን ያድሳታል፤ በእርጅናም ዘመንሽም ይጦርሻል፤ የምትወድሽና ከሰባት ወንዶች ልጆች የም ትበልጥብሽ ምራትሽ ወልዳዋለችና።"

[16]ከዚያም ኑኃሚን ሕፃኑን ተቀብላ ታቀ ፈችው፤ ሞግዚትም ሆነችው። [17]ጎረቤቶቿ የሆኑ ሴቶችም፣ "ለኑኃሚን ወንድ ልጅ ተወለደላት" አሉ። ስሙንም ኢዮቤድ ብለው ጠሩት፤ እርሱም የዳዊት አባት የሆ ነው የእሴይ አባት ነበር።

[18]እንግዲህ የፋሬስ ቤተ ሰብ ትውልድ ይህ ነው፦

ፋሬስ ኤስሮምን ወለደ፤
[19]ኤስሮምም አራምን ወለደ፤
አራምም አሚናዳብን ወለደ፤
[20]አሚናዳብም ነአሶንን ወለደ፤
ነአሶን ሰልሞንን[+] ወለደ፤
[21]ሰልሞንም ቦዔዝን ወለደ፤
ቦዔዝም ኢዮቤድን ወለደ፤
[22]ኢዮቤድም እሴይን ወለደ፤
እሴይም ዳዊትን ወለደ።

23፥10፤29፥16፤ 35፥16፤ዘዳ25፥9፤ ሩት1፥19
4፥12 ዘፍ38፥6፡24፡ 29
4፥13 ዘፍ8፥1፤29፥ 31፡32፤30፥6፤ ሉቃ1፥57
4፥14 ዘፍ24፥27፤ ሩት2፥20፤ሉቃ1፥58
4፥15 ዘፍ11፥31፤ 1ሳሙ1፥8፤2፥5፤ ኢዮ1፥2
4፥17 ቍ22፤1ሳሙ 16፥1፡13፡18፤17፥12፡ 58፤1ዜና2፥12፡13፡ 15፤መዝ72፥20
4፥18 ዘፍ38፥29፤ ዘኍ26፥21
4፥19 ዘፀ6፥23
4፥20 ዘኍ7፥12

[ሃ]15 አብዛኞቹ የዕብራይስጥ ቅጆች፣ ቡልጌትና ሱርስተ ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ አንዳንድ የዕብራይስጥ ቅጆች ግን ይነገረኛና ይላሉ።
[+]20 ጥቂት የዕብራይስጥ ቅጆች፣ አንዳንድ የሰብዓ ሊቃናትና ቡልጌት (እንዲሁም ቍጥር 21 እና ከሰብዓ ሊቃናት 1ዜና 2፥11 ይመ) ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ አብዛኞቹ የዕብራይስጥ ቅጆች ግን ሳልማ ይላሉ።

29 ይመ)። *ኤፍራታ፤* የ1፥2 ማብ ይመ።

4፥12 *ትዕማር ለይሁዳ እንደ ወለደችው እንደ ፋሬስ፤* ፋሬስ የቦዔዝ ዘር ነው (ቍ 18-21፤ ማቴ 1፥3፤ ሉቃ 3፥33 ይመ)፤ ፋሬስ ከይሁዳ ቤት ሊወለድ የቻለው አንድ ሰው ዘር ሳይተካ የሞተ እንደሆነ የሟቹን ሚስት ወንድሙ በመውረስ ዘር እንዲተካ በሚያዘው በሙሴ ሕግ መሠረት ነው (ዘፍ 38፡27-30፤ የ1፥11 ማብ ይመ)። እንግዲህ ፋሬስ ሽማግሌዎቹ ለቦዔዝ የሰጡ ትን ምርቃት በቦዔዝ ትውልድ በኩል ሊያገኝ ይችላል ማለት ነው። ከዚህ በተጨማሪ የፋሬስ ዘሮች የይሁዳ ነገድ በእስራ ኤል ሕዝብ መካከል ከፍ ከፍ እንዲል ትልቅ አስተዋፅኦ አድርገዋል። ስለዚህ የሽማግሌዎቹ ምርቃት ሩት ለቦዔዝ በምትወልድለት ልጅ በዳዊትና በሥርወ መንግሥቱ በኩል እውን ይሆናል። ቍ12 በምዕራፉ መደምደሚያ ላይ በአጭሩ የተነገረውን ለአንባቢው ከወዲሁ ያስተዋውቃል።

*4፥13-17፤* የታሪኩ መደምደሚያ ከታሪኩ መግቢያ ጋር ተመሳሳይ ነው (1፥1-5)፤ ይኸውም፣ (1) በዕብራይስጡ ሁለቱም ክፍሎች እኩል የቃላት ብዛት አላቸው፤ (2) ሁለቱም ረጅሙን ታሪክ በአጭሩ ያቀርባሉ፤ (3) ሁለቱም ክፍሎች በኑኃሚን ላይ ያተኮ ራሉ፤ (4) መግቢያው ኑኃሚን ባዶ እጇን እንደቀረች ሲናገር መደምደሚያው ደግሞ ሙላቷን ይናገራል።

4፥13 *እግዚአብሔር እንድትፀንስ አደረጋት፤* የ1፥6 ማብ ይመ።

4፥14 *የሚቤዥ ቅርብ የሥጋ ዘመድ፤* ቍ 15 ግልጽ እንደሚያደርገው ይህ ሕፃን ኢዮቤድ ነው። *ስሙ ይግነን፤* በቍ11 ላይ ይህ መልካም ምኞት ለቦዔዝ ተነግሮአል።

4፥15 *ከሰባት ወንዶች ልጆች የምትበልጥብሽ፤* 1ሳሙ 1፥8 ይመ። "ሰባት" ሙሉነትን ወይም ፍጹምነትን የሚያ መለክት ቍጥር በመሆኑ፣ ሰባት ወንዶች ልጆች የሚለው ለእስራ ኤል ቤት በሙሉ የተሰጠውን በረከት ባጭሩ የሚገልጽ ነው (1ሳሙ 2፥5፤ ኢዮ 1፥2፤ 42፥13 ይመ)። ሩት ለኑኃሚን ያሳየችው ፍጹም ታማኝነት እዚህ ላይ ከፍተኛ ቦታ ተሰጥቶታል።

4፥16 *ታቀፈችው፤* እንደ ራሷ ልጅ አድርጋ ልታሳድገው መቀበሏን ያመለክታል (የዘፍ 30፥3 ማብ ይመ)።

4፥17 *ለኑኃሚን ወንድ ልጅ ተወለደላት፤* ልጅ መውለድ የማትችለው አሮጊቷ ኑኃሚን በሩት አማካይነት በመሐሉን ምትክ ወራሽ ልጅ አገኘች። *ኢዮቤድ፤* የስሙ ትርጕም "አገልጋይ" ማለት ሲሆን፣ ስሙ ሙሉ ሆኖ ቢጻፍ ኖሮ "የእግዚ አብሔር አገልጋይ" የሚል ትርጕም አለው።

*4፥18-22፤* 1ዜና2፥5-15፤ ማቴ1፥3-6፤ሉቃ3፥31-33 ይመ። በዘፍ 5፥3-32፤11፥10-26 ላይ እንደሚገኘው የትውልድ ሐረግ ሁሉ በዚህ ክፍል የምናገኘውም የትውልድ ሐረግ ዐሥር ስሞች አሉት (የዘፍ 5፥5 ማብ ይመ)። ክፍሉ በዳዊት ዘመነ መንግሥት እስራ ኤል በተስፋዪቱ ምድር ያገኘችውን ሰላም (1ነገ5፥4 ይመ)፣ በ1፥1 ላይ ከተወሣውና በዘመነ መሳፍንት ከታየው ዕረፍት የለሽ ብጥብጥ ጋር ያነጻጽራል። ኑኃሚን በሩትና በቦዔዝ ጽኑ ፍቅር አማ ካይነት ከባዶነት ወደ ሙሉነት እንደመጣች ሁሉ፣ እግዚአብሔር የእስራኤልን ጦርነት በታማኝነት በተዋጋው በዳዊት በኩል ከብጥብጥ ወደ ሰላም አመጣ። ይህ የትውልድ ሐረግ የመጨረሻ ፍጻሜውን ያገኘው፣ የእግዚአብሔርን ሕዝብ ወደ ፍጹም ሰላም ባመጣው "በዳዊት ልጅ" በኢየሱስ ክርስቶስ ነው (ማቴ 1፥1)።

# መጽሐፈ ሳሙኤል - አንደኛ

## መግቢያ

### አሰያየሙ

በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ 1ኛ ሳሙኤልና 2ኛ ሳሙኤል የሚለው ስም የመጣው እግዚአብሔር በእስራ ኤል ምድር ንጉሣዊ አገዛዝን ለመመሥረት ከተጠቀመበት ሰው ጋር በተያያዘ ምክንያት ነው:: ሳሙኤል የመጀመሪያዎቹን ሁለቱን የእስራኤል ነገሥታት የቀባ ብቻ ሳይሆን፣ እግዚአብሔር በእስራኤል ላይ ያለውን አዲሱን ንጉሣዊ አስተዳደር የአመራር ስልት ያዋቀረ፣ መዋቅሩም ትርጉም እንዲያገኝ ያደረገ ሰው ነበረ:: ሳሙኤል በዚህኛው የእስራኤል ታሪክ ዋነኛው የእግዚአብሔር አገልጋይ ሆኖ መመረጡ ከሙሴ ጋር ያቀራርበዋል (መዝ 99፥6፣ ኤር 15፥1 ይመ)፣ ከመሳፍንት አገዛዝ ወደ ነገሥታት አገዛዝ በተደረገው ሽግግር፣ ሳሙኤል ከማንም ሰው ይልቅ ከፍ ያለ አስተዋፅአ ያደረገ ሰው ነበረ:: በመሠረቱ አንደኛ ሳሙኤልና ሁለተኛ ሳሙኤል እንደ አንድ መጽሐፍ የሚቈጠሩ ነበሩ፣ ሁለት ቦታ ተከፍለው፣ ሁለት መጽሐፍ የሆኑት ሰብዓ ሊቃናት (200 ዓ.ቅ.ክ. ገደማ) መጻሕፍተ ብሉያትን ከዕብራይስጥ ወደ ጽርዕ (ግሪክ) ቋንቋ በመለሱበት ጊዜ ነበር:: ከዚያ በኋላም ጀሮም የተባለው የላቲን ቤተ ክርስቲያን አባት ቅዱሳት መጻሕፍትን ወደ ሮማይስጥ (ላቲን) ቋንቋ በመለሰበት ጊዜ ይህንኑ ፈለግ በመከተል በሁለት ከፍሎታል:: ከዚያ በኋላ የተተርጐሙት ቅዱሳት መጻሕፍትም ወደ እኛ የደረሱት በዚሁ መልክ ነው::

### ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ፣ ጸሓፊውና የተጻፈበት ዘመን

የአንደኛ ሳሙኤልና ሁለተኛ ሳሙኤልን ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርይ፣ ጸሓፊውንና የተጻፈበትን ዘመን በተመለከተ አያሌ ጥያቄዎች ተነሥተዋል፣ መጽሐፉ የተዘጋጀው ራሳቸውን ከቻሉ የተለያዩ ምንጮች ለመሆኑ ከአንዳንድ የሥነ ጽሑፉ ባሕርያት መረዳት ይቻላል:: መጽሐፉ በተዘጋጀበትም ወቅት ጸሓፊው ከሌሎች ምንጮች በቀጥታ ሳይቀዳ በተቻለም መጠን ከመሠረታዊ ይዘቱ ሳያፋልስ እንዳለ በራሱ አቀራ ረብ አቀናጅቶ ሳይጽፈው እንዳልቀረ ይታመናል:: ጸሓፊው የንጉሥ ሰሎሞን ልዩ አማካሪ የነበረው ዛብድ ነው የሚሉ አሉ:: በእርግጥም ስለ ንጉሥ ዳዊት ዘመነ መንግሥት የሚያወሳ ዜና ከአባቱ፣ ከናታንና ከቤተ መንግሥቱ መዛግብት ማግኘት የሚችል ሰው ስለ መሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም፣ ብቻ ጸሓፊው ማንም ይሁን ከንጉሥ ሰሎሞን ሞት (930 ዓ.ቅ.ክ.) በኋላና እንዲሁም መንግሥቱ ከሁለት ከተከፈለ ("እስራ ኤልና ይሁዳ" የሚለውን አመለካከት ልብ ይሏል፣ በ11፥8፣ 17፥52፣ 18፥16፣ 2ሳሙ5፥5፣ 24፥1-9፣ ላይ የተጠቀሱትንና "የይሁዳ ነገሥታት" በሚል ጠንካራ አገላለጽ በ1ሳሙ27፥6፣ ላይ የተመለከተውን ይመ) በኋላ ጥቂት ቈየት ብሎ የእነርሱ ሰው ሳይሆን አይቀርም:: ጸሓፊው ከዚህም በቀር የሳሙኤልን፣ የሳኦልንና የዳዊትን ሕይወትና ዘመን በተመለከተ የተጻፉ መዛግብትን ሳያገላብጥ እንዳልቀረ እሙን ነው:: የያሳር መጽሐፍ ብቻ እንደ አንድ ምንጭ ተደርጎ በራሱ በመጽሐፉ ውስጥ በግልጽ ተመልክቶ አል (የያሳር መጽሐፍ፣ 2ሳሙ1፥18)፣ ይሁን እንጂ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ይህ ታሪክ ስለ ተፈጸመበት ዘመን፣ የሚናገሩ ሌሎች አራት መጻሕፍትን ጠቅሶአል (እነዚህም የዳዊት ዘመነ መንግሥት ታሪክ መጽሐፍ 1ዜና27፥24 የባለ ራእዩ የሳሙኤል የታሪክ መዛግብት፣ የነቢዩ የናታን የታሪክ መዛግብት፣ የባለ ራእዩ የጋድ የታሪክ መጻሕፍት 1ዜና29፥29 ናቸው)::

### የመጽሐፉ ይዘትና መሪ ሐሳብ

አንደኛ ሳሙኤል የነገሥታት አስተዳደር እንዴት በእስራኤል እንደ ተመሠረተ ይተርካል:: ጸሓ ፊው በመለኮታዊው አስተዳደር ውስጥ የተከሠተውን ፈጣን ለውጥ ከመግለጹ በፊትም የዐውዱን ውስብስብነት ያሳየናል:: የሚከተሉት ሁነቶች ስለ ንጉሣዊው አገዛዝ አጀማመር ታሪካዊና ትምህርተ መለኮታዊ ዐውዶችን ያቀርባሉ::

1. **የሳሙኤል ልደት፣ እድገትና መጠራት** (ም1-3):- በአብዛኛው ክፍሉ የመጀመሪያዎቹን ሁለት ነገሥታት የሳኦልንና የዳዊትን ታሪክ በሚያወሳ መጽሐፍ ጸሓፊው የሁለቱንም ነገሥታት ዜና ልደት ትቶ የእነርሱ ተቀዳሚ የነበረውንና ቅብዐ መንግሥት የቀባቸውን የነቢዩን የሳሙኤልን ልደትና እድገት ዘርዝሮ በመጻፉ ራሱን የቻለ አንድ የቍም ነገር ሥራ አከናውኖአል:: ይህ ራሱ ሳሙኤል ወደ ፊት ከሚፈጽማቸው ተግባሮች ጋር ጸሓፊው የያዘውን ቁም ነገር አስፈላጊነት ይበልጥ ያጕላብተዋል:: ሰዎች እንዲህ በቀላሉ ሊረዱት በማይችሉበት አገላለጽ የነገሥታት አገዛዝ ሥርዐት በሚመሠረትበት ሂደት ውስጥ ሥጋና ደም ለ"ቃል"እና ለ"መንፈስ" መገዛት ያለባቸው መሆኑን ሳይገልጽ እንዳልቀረ ይገመታል:: ንግሥና በመጀመሪያ ብቅ ያለው ከዚያም ያቈጠቈጠውና ሥር የሰደደው በነቢዩ በሳሙኤል የትንቢት ቃልና ሥራ ነው::

2. **ታቦቱን አስመልክቶ የሚያወሳው ታሪክ** (4-6):- ይህ ክፍል የአምላክ ታቦት በፍልስጥኤማውያን እንዴት እንደ ተማረከና እግዚአብሔር በፍልስጥኤም ከተሞች ላይ ታላቅ ጥፋት ካመጣ በኋላ ግን እን ዴት ወደ እስራኤል እንደ ተመለሰ በዝርዝር ያቀርባል:: እስራኤላውያን ታቦቱን ይዘው ለጦርነት መውጣታቸው ብቻ በጠላት ላይ ድል እንደሚያጐናጽፋቸው መተማመናቸው ስሕተት መሆኑን ትረካው በግልጽ ያሳየናል:: ይህም ብቻ አይደለም፣ እጅግ በተከበረውና አስደንጋጭ በሆነው በእስራኤል አምላክ

(የእግዚአብሔር ታላቅ ኀይል) ፊት የፍልስጥኤማውያን አምላክ ዳጎን እንደ ኢምንት እንኳ የማይቈጠር ከንቱ፣ የከንቱ ከንቱ መሆኑንም ከታሪኩ መረዳት ይቻላል። ፍልስጥኤማውያን የእስራኤልን ታቦት በመመለሳቸው የእግዚአብሔርን ኀይል ለመቋቋም የሚያስችላቸው ነገር አለመኖሩን ለመግለጽ ተገደዋል። የታቦቱን ውጣ ውረድ ዝርዝር ታሪክ በትክክል ስንመለከት እስራኤላውያን ያለማቋረጥ የሚታይ ንጉሥ በመፈለግ የምኞት ኀጢአት እንዲያድርባቸው በማድረጉ ረገድ የጐላ ሚና ተጫውቶአል።

3.**የሳሙኤል ምስፍናና ትድግና ምን**:- ሳሙኤል እስራኤላውያን ንስሓ እንዲገቡና ራሳቸውን እንደ ገና ለእግዚአብሔር እንዲያስገዙ አሳሰባቸው፤ በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር ረዳቸው፤ በፍልስጥኤማውያ ንም ላይ ድልን አቀዳጃቸው። ሳሙኤል በእግዚአብሔር ስለ ተመረጠ ሥልጣኑ ኀይል ያለው መሆኑንም ይህ ታሪክ ያረጋግጣል። እንዲሁም ሕዝቡ በእግዚአብሔር እስከ ታመነና የቃል ኪዳኑን ግዴታ አክብሮ ለመኖር ፈቃደኛ እስከ ሆነ ድረስ የእግዚአብሔር ጥበቃ እንደማይለየው ያስገነዝባል።

በም1-7 የተጻፈው ክፍል ንግሥና በእስራኤል እንዴት እንደ ተጀመረ በም8-12 ላይ ለተጻፈው ታሪክ እንደ መግቢያ ሆኖ ያገለግላል፤ እንደ መግቢያ ሆኖ ማገልገሉም ደግሞ አስፈላጊነት አለው። ጸሓ ፊው በም8-12 ላይ ያሉትን ታሪኮች አሳምሮ አቅርቦአቸዋል፤ ይህን ያደረገውም ታሪካዊ ክሥተቶቹን የከበቧ ቸው ዋና ዋናዎቹ የትምህርተ መለኮት ግጭቶች ይበልጥ ኀይል እንዲኖራቸው ነው። ምሁራን እነዚህን ምዕራፎች በማጥናት፣ ንጉሣዊ አገዛዝን በተመለከተ ሁለት ተቃራኒ ኀይሎች ግራና ቀኝ በመሆን ገመድ በሚጓተቱበት ጊዜ ያለውን ውጥረት የመሰለ ለመምረጥ የሚያስቸግር ሐሳብ እንዳለበት ለመረዳት ችለ ዋል። ሳሙኤል ለሕዝቡ ንጉሥ እንዲያነግሥ ከእግዚአብሔር ሲታዘዝ ይታያል (8፥7:9:22፤ 9፥16-17፤ 10፥24፤ 12፥13)፤ በሌላ በኩል ደግሞ ሕዝቡ ንጉሥ እንዲነግሥለት መጠየቁ እግዚአብሔርን እንደተወና ይህም ኀጢአት ሆኖ እንደተቈጠረበት ይታያል (8፥7፤ 10፥19፤ 12፥12:17:19-20)። ይህ የንግሥታቱን አገዛዝ በተመለከተ እርስ በርሱ የሚቃረን መስሎ የሚታየው ሐሳብ መግምገም ያለበት የእስራኤል ሕዝብ ከእግዚ አብሔር ጋር በነበረው የቃል ኪዳን ትስስር ይዘት አንጻር መሆን አለበት።

እስራኤል በዙሪያዋ እንዳሉት አሕዛብ አንድ ቀን የራሷን ንጉሥ የማንገሥ ፍላጎት ሳያድርባት እንደማይቀር ሙሴ ዐውቆና ተረድቶ ነበር (ዘዳ 17፥18-20)፤ ይሁን እንጂ በእስራኤል የሚመሠረተው ንጉሣዊ አገዛዝ ታላቁና እውነተኛው ንጉሣቸው ከሆነው ከእግዚአብሔር የፍትሕ ርትዕ አገዛዝ ጋር ተጣጥሞ መቀጠል አለበት፤ በዚህ ፈንታ ግን የእስራኤል ሽማግሌዎች ሳሙኤል ንጉሥ እንዲያነግሥላቸው በጠየ ቁት ጊዜ (8፥5:19-20)፣ በእነርሱ ላይ ነግሦ በርትዕ ፍትሕ ሲመራቸው፣ ሲያስተዳድራቸው የነበረውን የእ ግዚአብሔርን ንጉሥነት ናቁ፤ አቃለሉ (8፥7፤10:19፤ 12፥17:19)። በዙሪያቸው ያሉ አሕዛብ እንደሚያደርጉት ሁሉ በጦርነት ጊዜ መርቶ እንዲያወጣቸው፣ ለእስራኤል ጸጥታና ደኅንነት ምክንያት፣ ለአንድነቷም ማሰሪያ ሰንሰለት እንዲሆን ፈልገው ንጉሥ እንዲያነግሥላቸው መጠየቃቸው እውነተኛ ንጉሣቸው ከሆነው ከእግዚአብሔር ጋር ያስተሳሰራቸውን የቃል ኪዳን ገመድ ቈርጦ እንደ መጣል ይቈጠ ራል። ከዚህም ይልቅ እግዚአብሔር ተስፋ የሰጣቸው፣ ጋሻ መከታቸው መሆኑን ብቻ ሳይሆን፣ ስለ እነርሱ ሆኖ ኀይሉን በተደጋጋሚ እንደሚገልጥ አሳይቶአል፤ አሁን በቅርቡ እንኳ (በሳሙኤል ጊዜ ማለት ነው) ታቦቱን በተመለከተ የተፈጸመው ድርጊትና (ም4-6) በሳሙኤልም መሪነት በፍልስጥኤማውያን ላይ የተገኘው ድል (ም7) አለ።

ያም ሆኖ ግን ለሕዝቡ ንጉሥ ያነግሥላቸው ዘንድ እግዚአብሔር ሳሙኤልን አዘዘው (8፥7:9:22)። ሳኦል ከሳሙኤል ጋር እንዲገናኝ እግዚአብሔር ፈቀደ፤ ሳሙኤልም ሳኦልን ለብቻው ወስዶ ለንጉሥነት የሚያበቃውን ቅባት እንዲቀባው አዘዘው (9፥1-10፥16)። ከዚያም ሳሙኤል ሕዝቡን በምጽጳ ሰብስቦ፣ ንጉሥ እንዲነግሥላቸው መፈለጋቸው (10፥18-19) ኀጢአት መሆኑን አንሥቶ እንደ ገና ከወቀሳቸው በኋላ፣ ንጉሡን በዕጣ ለማስመረጥም ዋናው ሰው እርሱ ራሱ ሆነ፤ ዕጣው በሳኦል ላይ ወጣ፤ እግዚአብሔር የመረጠውም እርሱ መሆኑን ለሕዝቡ አሳወቀ (10፥24)። ሳኦል ይህ እንደ ሆነ ያኔውኑ የንጉሥነት ሥራ ውን አልጀመረም፤ በቀጥታ ወደ ቤቱ ሄደ ዕርሻውን ያርስ ጀመር (11፥5:7)። አሞናዊው ናዖስ የኢያቢስ ዘገለዓድ ሰዎች በፍርሀት እንዲዋጡ ባደረገ ጊዜ፣ "ሳኦል እኔ አለሁላችሁ" ብሎ ለመግጠም ሰራዊት አሰ ባሰበ፣ ወደ ጦር ግንባር ዘመተ፤ እስራኤልንም ድል አቀዳጀ። ጦርነቱን በድል አድራጊነት መወጣቱም ሳኦል እንዲነግሥ የእግዚአብሔር ፈቃድ ስለ መሆኑ የመጨረሻው ማረጋገጫ ማኅተም ሆነ (10፥24-12፥25 ይመ)።

እንግዲህ ዛሬም እንኳ ትክክለኛ መልስ የሚያሻው ጥያቄ በዚያን ጊዜ እስራኤል እስከዚህ ንጉሥ ያስፈልጋት ነበር ወይ? የሚል ነው። ንጉሥ እንዲኖራቸው የፈቀደ እግዚአብሔር ለመሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም፤ ይሁን እንጂ ዛሬ ምድራዊ ንጉሥ በላያቸው ማንገሥ ከጀመሩ፣ ራሱ ንጉሥ ሆኖ ያስተዳድራ ቸው ከነበረው ከእግዚአብሔር ጋር ያላቸው ቃል ኪዳን እንዴት አድርገው ሊጠብቁት ይችላሉ? የሳኦል በዓለ ንግሥ በተከበረበት ሰዓት፣ ሳሙኤል ሕዝቡ ንስሓ እንዲገባ፣ ከእግዚአብሔር ጋር ያለውንም ግንኙነት እንዲያድስ ያኔውኑ ባሳሰበ ጊዜ ይህ ችግር እንዲፈታ አድርጎአል (11፥14-12፥25፤ እንዲሁም የ10፥18-19 ማብ ይመ)።

ሳሙኤል ቃል ኪዳን አድሶ የንጉሥ አገዛዝ ሥርዐት ከመሠረተ በኋላ፣ በዙሪያው ካሉት የአሕዛብ ነገሥታት አገዛዝ ፈጽሞ ልዩ የሆነ ንጉሣዊ አስተዳደር በእስራኤል ምድር እንዲገኝ አድርጎአል። ንጉሥ በእስራኤል ምድር ያሻውን ሁሉ ማድረግ የሚችል ሳይሆን ሥልጣኑም፣ ኀይሉም በእግዚአብሔር ሕግና በነቢያት ቃል የተገደበ ነበር( 10፥25፤12፥23)፤ ይህም ሳኦልን ብቻ ሳይሆን፣ ከእርሱ በኋላ በእስራኤል

ዙፋን ላይ የሚቀመጡትን ነገሥታት ሁሉ የሚመለከት ሥርዐት ነበር፤ ሥርዐቱም ንጉሥ መሣሪያ ሆኖ እግዚአብሔር በእርሱ አማካይነት የገዛ ሕዝቡን የሚገዛበት፣ ሕዝቡም በበኩሉ እንደ ንጉሡ ሁሉ ፍ ጹም ገዥአቸው እግዚአብሔር መሆኑን ዐውቀው የሚገዙበት ሥርዐተ መንግሥት ነበር (12፥14-15)::

ሳኦል ግን በእግዚአብሔር የበላይነት የሚተዳደረው መንግሥት ለሚጠይቀው ሕግ መገዛት አለ መፈለጉን ያሳየው ወዲያውኑ ነበር (ም13-15):: የነቢዩን የሳሙኤልን ቃል ጥሶ ፍልስጥኤማውያንን ለመ ውጋት በተዘጋጀና (13፥13) አማሌቃውያንን ፈጽሞ እንዲያጠፋቸው በሳሙኤል አማካይነት የተነገረ ውን የእግዚአብሔር ቃል (ም15) ለመስማት ፈቃደኛ ባልሆነ ጊዜ፣ ሳኦል የእግዚአብሔር መሣሪያ መሆኑ ቀረ፤ ሕዝቡንም በእርሱ አማካይነት መግዛቱ አበቃ፤ አለመታዘዙም በእግዚአብሔር ዘንድ መናቅን አስከተለበት (15፥23)

ቀሪው የመጽሐፈ ሳሙኤል ቀዳማዊ ክፍል (ም16-31) ዳዊት በሳኦል ምትክ መመረጡን፣ እዚያ ቦታ ለመድረስም የተጓዘባቸውን አስቸጋሪ ጐዳናዎች የሚዘረዝር ነው:: የሳኦል አገዛዝ ከእግዚአብሔር መንገድ በየጊዜው እየወጣ መሄዱ ቢቀጥልም፣ ዳዊት መንግሥቱን በኀይል ሊቀማው አልፈለገም፤ ነገሩን ሁሉ ለእግዚአብሔር ተወው:: በኋላም ሳኦል ከፍልስጥኤማውያን ጋር ባደረገው ጦርነት ቈሰለ፤ በፍልስጥኤ ማውያን እጅ መውደቁን ስለፈራም በገዛ እጁ ራሱን ገደለ፤ ሦስቱ የሳኦል ወንዶች ልጆች በጦርነቱ ላይ ሞቱ:: ከነዚህም አንዱ የዳዊት የልብ ወዳጅ ዮናታን ነበር (ም3)

**የሁነቶች ቅደም ተከተል**

ምንም እንኳ የ1ኛ ሳሙኤልና የ2ኛ ሳሙኤል ታሪኮች አንዳንዶቹ የዘመናትን ቅደም ተከተል የጠበቁ ቢሆኑም (ለምሳሌ 1ሳሙ6፥1፤ 7፥2፤ 8፥1:5፤ 13፥1፤ 25፥1፤ 2ሳሙ2፥10-11፤ 5፥4-5፤ 14፥28፤ 15፥7 ይመ)፣ እንደ እውነቱ ግን ጥንቅር መረጃዎቹ የዚህኛውን ዘመን ዋና ዋናውን የእስራኤል ታሪክ ድርጊት ትክክለኛ የዘመናት ቅደም ተከተል ጠንቅቀው አስቀምጠዋል ለማለት ያስቸግራል:: በትክክል ከሚታወቀው (2ሳሙ5፥4-5)፣ ዳዊት ከተወለደበት ቀንና ከዘመነ መንግሥቱ ቍጥር ልክ በስተቀር፣ የቀረው የታሪክ ዘመናት ቅደም ተከተል እስከዚህ የጠነቀቀ አይደለም፤ ሳኦል ሲነግሥ ዕድሜው ስንት እንደ ነበርና የግዛት ዘመኑ የቈየበትንም ጊዜ ቅደም ተከተል መጽሐፉ ጠንቅቆ ባለ መመዝገቡ የተከሠተው ችግር የተወለደበትንና ነግሦ መግዛት የጀመረበትን ጊዜ በትክክል ላለማወቅ የራሱን አስተዋፅኦ አድርጎአል:: ስለ ሳሙኤል የልደትና (1ሳሙ 1፥1) የሞት ጊዜ የሚያስረዳ የተጻፈ ነገር የለም፤ ይኸስም ይብዛ በከፊል፣ ከሳምሶን እንዲሁም ከሩት ከተወለደው ከዳዊት አያት ከቦዔዝ ዘመን ሳይጋጠም አልቀረም:: የእስራኤል ሽማግሌዎች ንጉሥ እንዲነግሥላቸው በጠየቁት ጊዜ፣ ሳሙኤል ዕድሜው ገፍቶ እንደ ነበር የሚያመለክት ነገር አለ (8፥1:5 ይመ):: የታሪኩ ቅደም ተከተል በትክክል ሊቀመጥ ካል ቻለባቸው ምክንያቶች አንዱ፣ ራሱ ጸሓፊው ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻው ድረስ ላለው ለሌላው ድርጊት እንጂ ለታሪኩ ሂደት ቅደም ተከተል እስከዚህ ሥራዬ ብሎ ትኵረት አለመስጠቱ ነው::

ለምሳሌ 2ሳሙ 7፥1 በቅደም ተከተሉ መሠረት ቦታው አሁን ያለበት ሳይሆን በ2ሳሙ 8፥1-14 ላይ እንደ ተጻፈው የዳዊትን ድል ማድረግ ተከትሎ መምጣት አለበት (የ2ሳሙ 7፥1፤8፥1 ማብ ይመ ):: ሌላው ደግሞ፣ ሳኦል ከገባዖን ሰዎች ጋር ያደረገውን ውል ስላፈረሰ፣ በዳዊት ዘመን የተከሠተው ራብ ታሪክ ተጽፎ የሚገኘው በ2ሳሙ21፥1-4 ላይ ነው:: እንደ ታሪኩ ሂደት ቅደም ተከተል ግን፣ ይህ ታሪክ የተጻፈው በ2ሳሙ 15-18 ላይ እንደ ተጻፈው (2ሳሙ21፥1-2 ማብ ይመ)፣ አቤሴሎም ከማመፁ በፊት ነበር፤ ይሁን እንጂ ከዚህ የሚቀጥለው የጊዜ ሰሌት ይብዛም ይነስም የሳሙኤልንና የዳዊትን ዋና ዋና የጊዜ ቅደም ተከተል የሚያ መለክት ነው::

1105 ዓ.ቅ.ክ- ሳሙኤል የተወለደበት ዘመን (1ሳሙ 1፥20)
1080 ዓ.ቅ.ክ - ሳኦል የተወለደበት ዘመን
1050 ዓ.ቅ.ክ- ሳኦል ለንጉሥነት ተቀባ (1ሳሙ10፥1)
1040 ዓ.ቅ.ክ- ዳዊት የተወለደበት ዘመን
1025 ዓ.ቅ.ክ- ዳዊት በሳኦል ምትክ ተቀባ (1ሳሙ16፥1-13)
1010 ዓ.ቅ.ክ- ሳኦል ሞተ፤ ዳዊት በኬብሮን ተቀምጦ በይሁዳ ሁሉ ላይ ነገሠ (2ሳሙ 1፥1፤2፥1:4:11)
1003 ዓ.ቅ.ክ- ዳዊት መላውን እስራኤልን ጠቅልሎ ገዛ፤ ኢየሩሳሌምንም ያዘ (2ሳሙ5)
997-992 ዓ.ቅ.ክ- ዳዊት የተዋጋቸው ጦርነቶች (2ሳሙ8፥1-14)
991 ዓ.ቅ.ክ- ሰሎሞን ተወለደ (2ሳሙ 12፥24፤1ነገ3፥7፤11፥42)
980 ዓ.ቅ.ክ- ዳዊት ሕዝቡ እንዲቈጠር አደረገ (2ሳሙ 24፥1)
970 ዓ.ቅ.ክ- የዳዊት ዘመነ መንግሥት ፍጻሜ (2ሳሙ 5፥4-5፤ 1ነገ 2፥10–11)

**አስተዋፅኦ**

1. ንጉሥነት በእስራኤል እንዲመሠረት ያመቻቹ የታሪክ ቅደም ተከተል ሁኔታዎች ጅማሬ (1ሳሙ1-7)
   ሀ) የሳሙኤል ልደት፣ ወጣትነቱና ለነቢይነት መጠራቱ፤ በዔሊ ቤት ላይ የተወሰነ ፍርድ (1ሳሙ1-3)
   ለ) እስራኤል በፍልስጥኤማውያን ድል ሆነች፤ የእግዚአብሔር ታቦት ተማረከ፤ ተመለሰ፤ ሳሙኤል ዳኛና ታዳጊ በመሆን ያከናወናቸው ሥራዎች( 1ሳሙ4-7)
2. በነቢዩ በሳሙኤል አመራር ንጉሥነት በእስራኤል ተመሠረተ (1ሳሙ 8-12)

ሀ) ሕዝቡ ንጉሥ እንዲኖረው ጠየቀ፤ ይህም ኀጢአት ነበር። እግዚአብሔርም ንጉሥ እንደሚያነግሥ ባቸው (እንደሚሰጣቸው) ፈቃዱ መሆኑን ገለጠ (1ሳሙ 8)።
ለ) ሳሙኤል ሳኦል ንጉሥ ይሆን ዘንድ ቀባው (1ሳሙ 9፥1-10፥16)
ሐ) ሳኦል ንጉሥ ይሆን ዘንድ ብዙ ሕዝብ ባለበት በምጽዳ ዕጣ ወጣለት (1ሳሙ 10፥17-27)
መ) ሳኦል ለንጉሥነት የመመረጡ ነገር፣ በአሞናውያን ላይ ባገኘው ድል ተቀባይነት አገኘ (1ሳሙ 11፥1-13)
ሠ) ሳሙኤል በጌልጌላ ላይ ሕዝቡን ሰብስቦ ቃል ኪዳኑን ባደሰበት ቀን፣ የሳኦል ንጉሥነት በታላቅ ሥነ ሥርዐት ተከበረ (1ሳሙ 11፥14-12፥25)

3. የሳኦል አገዛዝ ውድቀት (1ሳሙ 13-15)
4. ዳዊት በዙፋኑ ላይ ተቀመጠ፤ የሳኦል መንግሥት በተከታታይ ኀይሉና ብርታቱ እየቀነሰና እየተዳከመ ሄደ፤ በመጨረሻም ወደቀ (1ሳሙ 16፥1-2ሳሙ 5፥5)፤
ሀ) ዳዊት ተቀባ፤ ንጉሥ ሳኦልን በወታደርነት አገለገለ፤ ሕይወቱን ለማትረፍ ሸሸ፤ (1ሳሙ 16-26)
ለ) ዳዊት በፍልስጥኤም ምድር ጥገኛ ሆነ፤ ሳኦልና ወንዶች ልጆቹ በጦርነት ላይ ሞቱ (1ሳሙ 27-31)
ሐ) ዳዊት በይሁዳ ላይ ነገሠ (2ሳሙ 1-4)
መ) ዳዊት በመላው እስራኤል ላይ ነገሠ (2ሳሙ 5፥1-5)
5. ዳዊት ያከናወናቸው ሥራዎችና ያገኘው ታላቅ ክብር (2ሳሙ 5፥6-9፥12)
ሀ) ዳዊት ኢየሩሳሌምን ድል አድርጎ ያዛት፤ ፍልስጥኤማውያንንም አሸነፈ (2ሳሙ 5፥6-25)
ለ) ዳዊት ታቦቱን ወደ ኢየሩሳሌም አመጣ (2ሳሙ 6)
ሐ) እግዚአብሔር ለዘላለም ጸንቶ የሚኖር ሥርወ መንግሥት ለዳዊት እንደሚሰጠው ቃል ኪዳን ገባለት (2ሳሙ 7)።
መ) የዳዊት መንግሥት ሰፋ፤ በውስጥ አስተዳደሩም ፍትሕ ሰፈነ (2ሳሙ 8)
ሠ) ዳዊት ከዮናታን ጋር የገባውን ቃል ኪዳን እስከ መጨረሻው ጠበቀ (2ሳሙ 9)
6. የዳዊት ዘመነ መንግሥት ድክመቶችና ውድቀቶች (2ሳሙ 10-20)
ሀ) ዳዊት የዝሙት በደል ፈጸመ፤ነፍስም አጠፋ (2ሳሙ 10-12)
ለ) ዳዊት ልጆቹን አምኖንንና አቤሴሎምን በሞት አጣ (2ሳሙ 13–20)
7. የመጨረሻው የዳዊት ዘመነ መንግሥት ገጽታ (2ሳሙ 21-24)

## የሳሙኤል መወለድ

**1** በተራራማው በኤፍሬም አገር በአርማቴም መሴፋ የሚኖር ሕልቃና የተባለ አንድ ሰው ነበረ፤ እርሱም ኤፍሬማዊ ሲሆን፣ የኢያሬምኤል ልጅ፣ የኢሊዩ ልጅ፣ የቶሑ ልጅ፣ የናሲብ ልጅ፣ ነበረ። [2]እርሱም አንዲቱ ሐና፣ ሌላዪቱ ፍናና የተባሉ ሁለት ሚስቶች ነበሩት፤ ፍናና ልጆች ሲኖሯት፣ ሐና ግን ምንም ልጅ አልነበራትም።

[3]ያም ሰው ሁሉን ቻይ ለሆነው ለእግዚአብሔር ለመስገድና መሥዋዕት ለመሠዋት በየዓመቱ ከሚኖርበት ከተማ ወደ ሴሎ ይወጣ ነበር። በዚያም ሁለቱ የዔሊ ልጆች አፍኒንና ፊንሐስ የእግዚአብሔር ካህናት ነበሩ። [4]ሕልቃና ወደ ሴሎ ሄዶ መሥዋዕት የሚሠዋበት ወቅት በደረሰ ጊዜ ሁሉ፣ ለሚስቱ ለፍናና እንዲሁም ለወንዶችና ለሴቶች ልጆቿ ሁሉ ከሥጋው ድርሻቸውን ይሰጣቸው ነበር። [5]ሐናን ግን ይወዳት ስለ ነበር፣ ዕጥፍ ድርሻ ይሰጣት ነበር፤ ይሁን እንጂ እግዚአብሔር ማሕፀኗን ዘግቶት ነበር። [6]እግዚአብሔር ማሕፀኗን ስለ ዘጋም ጣውንቷ ታስቈጣት፣ ታበሳጫትም ነበር። [7]ይህም በየዓመቱ ይደጋገም ነበር፤ ሐና ወደ እግዚአብሔር ቤት በምትወጣበት ጊዜ ሁሉ፣ እስክ ታለቅስና መብላት እስኪያቅታት ድረስ ጣውንቷ ታበሳጫት ነበር። [8]ባሏ ሕልቃናም እርሷን፣ "ሐና ሆይ፤ ለምን ታለቅሻለሽ? ለምንስ አትበዪም? ልብሽስ ለምን ያዝናል? ከዐሥር ወንዶች ልጆች እኔ አልበልጥብሽምን?" ይላት ነበር።

[9]አንድ ጊዜ በሴሎ ሳሉ ከበሉና ከጠጡ በኋላ ሐና ተነሥታ ቆመች፤ በዚያ ጊዜ ካህኑ ዔሊ በእግዚአብሔር ቤት መቅደስ[u] መቃን አጠገብ በወንበር ላይ ተቀምጦ ነበር። [10]ሐናም በነፍሷ ተመርራ አብዝታ በማልቀስ ወደ እግዚአብሔር ጸለየች። [11]እንዲህም ብላ ስእለት ተሳለች፤ "የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ሆይ፤ የአገልጋይህን መዋረድ ተመልክተህ ብታስበኝና አገልጋይህን ሳትረሳት ወንድ ልጅ ብትሰጣት፣ በሕይወት ዘመኑ ሁሉ ለእግዚአብሔር እሰጠዋለሁ፤ ምላጭም በራሱ ላይ አይደርስም።"

[12]ሐና ባለማቋረጥ ወደ እግዚአብሔር በጸለየች ጊዜ፣ ዔሊ አፏን ይመለከት ነበር። [13]እርሷም በልቧ ትጸልይ ስለ ነበር፣ ከንፈሯ ይንቀሳቀስ እንጂ ድምጿ አይሰማም ነበር፤ ዔሊም እንደ ሰከረች አድርጎ ቈጠራት [14]እርሱም "ስካሩ የማይለቅሽ እስከ መቼ ድረስ ነው? የወይን ጠጅሽን ከአንቺ አስወግጂው" አላት።

[15]ሐናም እንዲህ ብላ መለሰችለት፤ "ጌታዬ

1፥1 ኢያ 17፥17-18፤ 25፥21፥20-22
1ሳሙ 9፥5፤
1ዜና 6፥27፡34
1፥2 ዘፍ 4፥19
1፥3 ቍ21፤
ዘፀ23፥14፤
ዘዳ12፥5-7፤
ኢያ18፥1፤
1ሳሙ 2፥19፤31፤
14፥3፥20፥6፥29፤
ሉቃ2፥41
1፥4 ዘፍ29፥34፤
ዘሌ7፥15-18፤
ዘዳ12፥17-18
1፥5 ዘፍ11፥30፤
29፥31፥37፥3
1፥6 ዘፍ16፥4
1፥7 2ሳሙ12፥17፤
መዝ102፥4
1፥8 ሩት4፥15
1፥9 1ሳሙ3፥3
1፥10 ኢዮ3፥20፤
7፥11፥10፥1፥21፥25፤
23፥2፥27፥2፤
ኢሳ38፥15፤
ኤር 20፥18
1፥11 ዘፍ 8፥1፤
17፥1፤ዘኍ6፥1-21፤
መሳ11፥30፥13፥5፡7፤
መዝ24፥10፥46፥7፤
ኢሳ 1፥9፤ሉቃ1፥15
1፥15 2ነገ4፥27፤
መዝ42፥4፤
62፥8፤ሰቆ2፥19

[u]9 የማደሪያ ድንኳን ማለት ነው

1፥1 *በአርማቴም፤* ይህ ስም በብሉይ ኪዳን ውስጥ የሚገኘው እዚህ ላይ ብቻ ነው፤ "ራማ" ለሚለውም ስም ሌላው መጠሪያ ነው (1፥19፤ 2፥11፤ 7፥17፤ 19፥18፤ 25፥1 ይመ)። ምናልባትም ከኢየሩሳሌም በስተ ሰሜን ከኤፍሬምና ከብንያም ድንበር ስምንት ኪሎ ሜትር ርቃ ከምትገኘው ከኵረብታማዋ አገር ከብንያም ራማ (ኢያ 18፥25 ይመ) ጋር ሳትመሳሰል አትቀርም። *የናሲብ፤* ይህ ስም ሰውንም ሆነ ቦታን የሚያመለክት ስለ መሆኑ በውል የሚታወቅ ነገር የለም። ሰውን የሚመለከት ከሆነ ናሲብ የተባለውን ዘር (1ዜና 6፥34-35)፣ ቦታን የሚያመለክት ከሆነ ደግሞ አርማቴም የተባለውን አካባቢ ያመለክታል (9፥5 ይመ)። *ኤፍሬማዊ፤* በዚህ ስፍራ ሕልቃና ኤፍሬማዊ ተብሎ ቢጠራም፣ ምናልባት ቤተሰቡ በኤፍሬም፣ ከተሞች ተሰጥተውት ከነበረው ከቀሃት ነገዶች የተገኘ ሌዋዊ ሳይሆን አይቀርም (ኢያ 21፥20-21፤ 1ዜና 6፥22-26 ይመ)።

1፥2 *ሁለት ሚስቶች፤* የዘፍ 4፥19፥16፥2፥25፥6 ማብ ይመ።

1፥3 *በየዓመቱ ... ይወጣ ነበር፤* ወንድ የሆነ ማንኛውም እስራኤላዊ በዓመት ሦስት ጊዜ በእግዚአብሔር ፊት ለመቅረብ ወደ ቤተ መቅደስ መሄድ አለበት (ዘፀ 23፥14-19፤ 34፥23፤ ዘዳ16፥16-17 ይመ)። እዚህ ላይ የተጠቀሰው በዓል የዳስ በዓል ሳይሆን አይቀርም። ይህ በዓል የሚከበረው ከምድረ በዳ ወደ ከነዓን በተደረገው ጕዞ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ስላደረገው እንክብካቤ ብቻ ሳይሆን (ዘሌ23፥43)፣ ይበልጡኑ በዚሁ ዓመት እግዚአብሔር ሕዝቡን በእህል አዝመራ መባረኩን በማሰብ ጭምር በደስታና በፈንጠዝያ የሚከበር በዓል ነው (ዘዐ16፥13-15)። እንዲህ ያለ ታላቅ በዓል በሚከበርበት ጊዜ ሐና መካን በመሆኗ በጠለቀ ሐዘን ውስጥ መገኘቷ እጅግ ልብን የሚነካ ነው። *ሁሉን ቻይ ለሆነው ለእግዚአብሔር፤* በሌላ አገላለጽ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ማለት ነው። እግዚአብሔር ለመጀመሪያ ጊዜ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ራሱን የገለጠበት ስም ነው። "ሰራዊት" የሚለው ቃል በዕብራይስጡ፣ (1) የጦር ሰራዊትን (ዘፀ 7፥4፤ መዝ 44፥9፤) (2) ሰማያውያን ፍጥረትን ማለትም ፀሓይን፣ ጨረቃንና ከዋክብትን (ዘፍ2፥1፤ዘዳ4፥19፤ኢሳ40፥26 ወይም (3) ልዩ ፍጥረታትን ማለትም መላእክትን (ኢሳ5፥14፤1ነገ 22፥19፤ መዝ 148፥2) የሚያመለክት ሊሆን ይችላል። "የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር" የሚለው ስም በፍጥረተ ዓለማት ውስጥ ባሉት ፍጥረታት ሁሉ የእግዚአብሔርን ሉዓላዊነት ያሳያል። እስራኤላውያን የንጉሥን አስተዳደር ከመፈለጋቸው ጕዳይ ጋር ሲያያዝ እግዚአብሔር በሰማይ ሰራዊትና (ዘዐ33፥2፤ኢያ5፥14፤መዝ68፥17፤ዕን 3፥8) በእስራኤል ሰራዊት (1ሳሙ 17፥45) ላይ "ጌታ ነው" መባሉ ትክክለኛ ይሆናል። *ሴሎ፤* መቅደስና የቃል ኪዳኑ ታቦት የተቀመጡበት በቤቴልና በሴኬም መካከል ያለ በኤፍሬም ውስጥ የሚገኝ ከተማ ነው (ኢያ18፥1፤መሳ 21፥9)።

1፥4 *መሥዋዕት፤* እዚህ ላይ የተጠቀሰው መሥዋዕት ከእግዚአብሔር ጋር ያለውን ኅብረትና አንድነት የሚመለከት ሲሆን፣ ስላደረገውም ምሕረት እርሱን በማመስገን የሚደረግ የደስታ መብል ነው (ዘሌ7፥11-18፤ ዘዐ12፥7፡17-18)።

1፥5 *እግዚአብሔር ማኅፀኗን ዘግቶት ነበር፤* ልጆችን የሚሰጥም ሆነ የሚነሣ እግዚአብሔር ነው (ዘፍ18፥10፤ 29፥31፤ 30፥2፡22)።

1፥6 *ጣውንቷ፤* የዘፍ16፥4ማብ ይመ።

1፥9 *ቤተ መቅደስ፤* እዚህና በ3፥3 ላይ የተጠቀሰው ማደሪያ "የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ" የሚል መጠሪያ ተሰጥቶታል፤ ደግሞም "የእግዚአብሔር ቤት" (ቍ7፥3፥15)፣ "የመገናኛው ድንኳን" 2፥22)፣ "መኖሪያዬ" (2፥32) ተብሎአል። ማደሪያው "ቤት"፣ "ቤተ መቅደስ" መባሉና በተጨማሪም መቃን ከፍሎችና በሮች በውስጡ መኖራቸው (3፥2፡15)፣ በዚህ ጊዜ ማደሪያው ትልቅና ቋሚ ሕንጻዎች መካከል መሆኑን ሲያመለክት፣ "ቤተ መቅደስ" መባሉ ትክክል ነው (ከኤር 7፥12፡14፡26፥6 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥11 *ተሳለች፤* ዘፍ28፥20-22፤ ዘኍ21፥2፤መዝ50፥14፤ 76፥11፤116፥14፡18፤ 132፥2-5፤ ምሳ20፥25፤ 31፥2 ይመ። ሴቶች እንዴት መሳል እንዳለባቸው የሚገልጽ መመሪያ በዘኍ 30 ላይ ይገኛል። *ተመልክተህ፤* ሐና ያለችበትን ሁኔታ እንዲሁ ከማየት ያለፈ ነው (ቍ19፤ የዘፍ8፥1 ማብ ይመ)። *በሕይወት ዘመኑ ሁሉ፤* አንድ ሌዋዊ ከ25 ዓመት ዕድሜው ጀምሮ መላ ሕይወቱን ለአገልግሎት የሚሰጥበትን ሁኔታ ያመለክታል (ዘኍ 8፥23-26 ይመ)። *ምላጭም በራሱ ላይ አይደርስም፤* ሐና፣ እግዚአብሔር ስለ ሶምሶን የተናገረውን ዐይነት ስእለት ተሳለች (መሳ 13፥5)። ረጅም ጠጕር ለጌታ አገልግሎት መለየትን የሚያመለክትና ከናዝራዊነት ስእለት አንዱ መታወቂያ ነው (ዘኍ 6፥1-21 ይመ)። ይህ ስእለት ለተወሰነ ጊዜ የሚፈጸም እንጂ የዕድሜ ልክ ስእለት አይደለም።

*1፥13 ሰክረች፤* እዚህ ላይ ዔሊ የፈጸመው ስሕተት በዚያ ዘመን የሰከሩ ሰዎች ወደ ቤተ መቅደስ መግባት የሚፈቀድላቸው መሆኑን ያመለክታል፤ የጊዜው ሃይማኖታዊና ግብረ ገባዊ አቋም የተበላሸ እንደ ነበረ የሚጠቍም ተጨማሪ ማስረጃ በመሳ 17፥21 ባሉት ታሪኮች ይገኛል።

ሆይ፤ ሰክሬ አይደለም፤ እኔ ልቧ ክፉኛ የታወከባት ሴት ነኝ፤ ልቤን በእግዚአብሔር ፊት አፈሰስሁ እንጂ፣ የወይን ጠጅም ሆነ ሌላ የሚያሰክር መጠጥ አልጠጣሁም:: [16]ይህን ያህል ጊዜ የጸለይሁት ከባድ ከሆነው ጭንቀቴና ሐዘኔ የተነሣ ስለ ሆነ፣ አገልጋይህን እንደ ምናምንቴ ሴት አት ቍጠረኝ::"

[17]ዔሊም፣ "በሰላም ሂጂ፤ የእስራኤል አምላክ የለመንሺውን ይስጥሽ" ሲል መለሰላት::

[18]እርሷም፣ "አገልጋይህ በፊትህ ሞገስ ታግኝ" አለች፤ ከዚያም መንገዷን ሄደች፤ ምግብም በላች፤ ከዚያም በኋላ በፊቷ ላይ ሐዘን አልታየም::

[19]በማግስቱ ጠዋት ተነሥተው *በእግዚ አብሔር* ፊት ሰገዱ፤ ከዚያም በራማ ወደ ሚገኘው ቤታቸው ሄዱ:: ሕልቃና ከሚስቱ ከሐና ጋር ተኛ፤ *እግዚአብሔርም* አሰባት፤ [20]ስለዚህ ሐና ፀነሰች፤ የእርግዝናዋ ወራት በተፈጸመ ጊዜም ወንድ ልጅ ወለደች፤ ስሙንም፤ "ከእግዚአብሔር ለምኜዋለሁ" ስትል ሳሙኤል[ሀ] አለችው::

## ሐና ሳሙኤልን ለእግዚአብሔር ሰጠች

[21]ሰውየውም ሕልቃና *ለእግዚአብሔር* ዓመታዊውን መሥዋዕት ለመሠዋት ስእለቱን ለማድረስ ቤተሰቡን ሁሉ ይዞ ወደ ሴሎ ወጣ:: [22]ሐና ግን አልሄደችም፤ እርሷም ባሏን፣ "ሕፃኑ ጡት ከተወ በኋላ፣ ወስጄ *በእግዚአብሔር* ፊት አቀርበዋለሁ፤ እስከ ሕይወቱ ፍጻሜም በዚያ ይኖራል" አለችው::

[23]ባሏ ሕልቃናም፣ "መልካም መስሎ የታየሽን አድርጊ፤ ጡት እስክታስጥዪው ድረስ እዚሁ ቆዪ፤ ብቻ *እግዚአብሔር* ቃሉን[ለ] ያጽናልሽ" አላት:: ስለዚህ ሐና ሕፃኑን ጡት እስክታስጥለው ድረስ እያጠባችው በቤቷ ተቀመጠች::

[24]ልጁ ጡት በተወ ጊዜ ከእርሱ ጋር አንድ የሦስት ዓመት ወይፈን[ሐ]፣ አንድ የኢፍ መስፈሪያ[መ] ዱቄትና አንድ አቍማዳ የወይን ጠጅ ወስዳ፣ በሴሎ ወዳለው ወደ *እግዚአብሔር* ቤት አመጣችው፣ ልጁም ገና ሕፃን ነበረ:: [25]ወይፈኑን ካረዱ በኋላም ልጁን ወደ ዔሊ አቀረቡት:: [26]ሐናም ዔሊን እንዲህ አለ ችው፤ "ጌታዬ ሆይ፤ በነፍስህ እምላለሁ፤ እዚህ ቦታ ላይ በአጠገብህ ቆማ ወደ *እግዚ አብሔር* ስትጸልይ የነበረች ያች ሴት እኔ ነኝ:: [27]ይህን ልጅ እንዲሰጠኝ ጸለይሁ፤ *እግዚ አብሔርም* የለመንሁትን ሰጠኝ:: [28]ስለዚህ እኔም *ለእግዚአብሔር* እሰጠዋለሁ፤ በሕይ ወት ዘመኑም ሁሉ *ለእግዚአብሔር* የተሰጠ ይሆናል::" እርሱም በዚያ *ለእግዚአብሔር* ሰገደ::

## የሐና የምስጋና ጸሎት

**2** ሐናም እንዲህ ብላ ጸለየች፤
"ልቤ *በእግዚአብሔር* ጸና፤
ቀንዴም[ሠ] *በእግዚአብሔር* ከፍ ከፍ አለ፤
አፌ በጠላቶቼ ላይ ተከፈተ፤
በማዳንህ ደስ ይለኛልና::
[2]"እንደ *እግዚአብሔር* ያለ ቅዱስ[ረ] ማንም
የለም፤
ከአንተም በቀር ሌላ የለም፤
እንደ አምላካችን ያለ ዐለት የለም::
[3]"ይህን ያህል በመታበይ አትናገሩ፤
እንዲህ ያለውም የእብሪት ቃል

1፥16 መዝ 55፥2
1፥17 ዘኍ25፥20፥21፤ ዘኁ 6፥26፤ 1ሳሙ 20፥42፤ 2ነገ5፥19፤ መዝ20፥3-5፤ ሐሥ15፥33
1፥18 ዘፍ18፥3፤ ሩት2፥13፤ሮሜ15፥13
1፥19 ዘፍ8፥1፤ 29፥31፤ኢሱ18፥25
1፥20 ዘፍ17፥19፤ 29፥32፤30፥6፤ ዘፀ2፥10፤ 1ሳሙ7፥5፤12፥23፤ 1ዜና6፥27፤ኤር15፥1፤ ማቴ1፥21፤ ዕብ11፥32
1፥21 ቍ3፤ ዘፍ28፥20፤ ዘኁ 30፥2፤ ዘዳ12፥11
1፥22 ዘፀ13፥2፤ ሉቃ2፥22
1፥23 ዘፍ21፥8፤ 25፥21
1፥24 ዘኍ15፥8-10
1፥27 1ሳሙ2፥20፤ መዝ66፥19-20
1፥28 መሳ13፥7
2፥1 ዘኁ10፥35፤ መዝ6፥8፡10፤13፥5፤1፤ 18፥2፤33፥21፤89፥17፡ 24፤148፥14፤ዘካ10፥7፤ ሉቃ1፥46-55
2፥2 ዘፍ49፥24፤ ዘፀ8፥10፤15፥11፤33፥22፤ ዘሌ11፥44፤ዘዳ32፥37፤ 2ሳሙ22፥2፡32፤23፥3፤ መዝ31፥3፤71፥3፤ ኢሳ40፥25፤46፥5
2፥3 ኢሳ22፥22፤ 1ሳሙ16፥7፤1ነገ8፥39፤ 1ዜና28፥9፤ 2ዜና6፥30፤ መዝ17፥10፤31፥18፤ 73፥8፤75፥4፤94፥4፤ ምሳ15፥11፤ 16፥2፤ 24፥11-12፤ ኤር11፥20፤17፥10

[ሀ]20 በዕብራይስጡ ሳሙኤል የሚለው ቃል ድምፅ *እግዚአብሔር ሰማ* ከሚለው ሐረግ ጋር ይመሳሰላል::
[ለ]23 የሙት ባሕር ጥቅል፣ የሰብዓ ሊቃናትና የሱርስቱ ትርጕም ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን *ቃልሽን* ይላል::
[ሐ]24 የሙት ባሕር ጥቅልል፤ የሰብዓ ሊቃናትና የሱርቱ ትርጕም ከዚህ፤ ጋር ይስማማል የማስሬቱ ቅጅ ግን *ሦስት ወይፈን* ይላል::
[መ]24 22 ሊትር ያህል ነው::
[ሠ]1 በዚህ ስፍራና በቍጥር 10 ላይ *ቀንድ* የጥንካሬ ምልክት ነው
[ረ]2 ወይም *አንድ ቅዱስ*

1፥16 *ምናምንቴ፤* የዘዳ13፥13 ማብ ይመ::

1፥20 *ሳሙኤል፤* እግዚአብሔር ሰማኝ ማለት ነው::

1፥21 *ዓመታዊ መሥዋዕት፤* የቍ3-4 ማብ ይመ:: *ስእለ ቱን፤* በብሉይ ኪዳን ምስጋና ለማቅረብ ለእግዚአብሔር የተገባ ውን ስእለት መፈጸም የተለመደ የሃይማኖት ሥርዐት ነበረ (ዘሌ 7፥16፤ መዝ 50፥14፤ 56፥12፡66፥13-15፤ 116፥17-18፤ ኢሳ 19፥21):: በዚህም መሠረት ሕልቃና እንደማንኛውም ሰው እግዚ አብሔር እህሉንና ከብቱን እንዲባርክለት ተስሎ፣ ስእለቱ ከደ ረሰለት በኋላ በዓመቱ የቂጣ በዓል ላይ ምስጋና ሊያቀርብ ሳይ መጣ አልቀረም (የቍ 3 ማብ ይመ)::

1፥22 *ጡት ከተወ በኋላ፤* በምሥራቁ ዓለም አንድን ሕፃን ሦስት ዓመት ወይም ከዚያ በላይ የእናቱን ጡት እንዲጠባ ማድ ረግ የተለመደ ነበር::

1፥23 *ቃሉን፤* እግዚአብሔር ከዚህ በፊት የተናገረው ቃል አልተጠቀሰም፤ ምናልባት ዔሊ በቍ17 ላይ የተናገረውን የሚመ ለከት ሊሆን ይችላል::

1፥26 *በነፍስህ እምላለሁ፤* የተናገሩትን ቃል እውነተኛነት ለማስረገጥ የሚነገር፣ የተለመደ ሐረግ ነው::

2፥1 *ጸለየች፤* የሐና ጸሎት፣ "የጸሎት መዝሙራት" እንደ ሚባሉት እንደ ዳዊት መዝሙራት ሁሉ፣ ለእግዚአብሔር የሚቀ ርብ የውዳሴና የምስጋና መዝሙር ነው (መዝ 72፥20):: የማር ያም የምስጋና ጸሎት (ሉቃ1፥46-55) "የአዲስ ኪዳን የምስጋና ቅኔ" እንደሚባል ሁሉ፣ ይህም ተመሳሳይ በመሆኑ አንዳንድ ጊዜ "የብሉይ ኪዳን የምስጋና ቅኔ" ተብሎ ይጠራል፤ ከዘካርያስ የቡ ራኬ መዝሙር ጋርም የሚመሳሰልበት መንገድ አለው (ሉቃ 1፥67-79):: የሐና የምስጋና መዝሙር በሁለተኛ ሳሙኤል መጨረሻ ላይ በሚገኘው የዳዊት መዝሙር ውስጥ በብዛት ተስተጋብቶአል (2ሳሙ 22):: በዚህ ስፍራና በ2ሳሙ22 ያሉት መዝሙሮች የመጽሐፉን ታሪክ ዋና ሐሳብ ሲያመለክቱ፣ የእግዚ አብሔርን መንገድ በማሳየት ምስጋናና ውዳሴ ላይ ያተኵራሉ:: ሐና በጸሎቷ እስራኤል ስለምትገባበት አዲስ ሕይወትና በልጇ በሳ ሙኤል በኩልም ስለሚመሠረተው ንጉሣዊ አስተዳደር ትንቢት ትናገራለች:: *ልቤ በእግዚአብሔር ጸና፤* የሐና በእግዚአብሔር መደገፍ የተመሠረተው ባገኘችው ልጅ ሳይሆን፣ ጸሎቷን በመለሰላት በእግዚአብሔር ላይ ነው:: *ቀንዴ ... ከፍ ከፍ አለ፤* ከዘዳ 33፥17፤ መዝ 75፥5፡10፤ 92፥10፤112፥9፤ ሉቃ1፥69 ጋር ያነጻጽሩ:: ቀንድ በእግዚአብሔር ከፍ ከፍ ሲል፣ አንድ ሰው ከውርደት ወደ ክብርና ኀይል ተሻልፎአል ማለት ነው::

2፥2 *ከአንተም በስተቀር ሌላ የለም፤* 2ሳሙ 7፥22፤ ዘፀ 4፥39፤ኢሳ45፥6ይመ:: *ዐለት፤* ይህ በዘይቤያዊ አገላለጽ የቀረበው ቃል የእስራኤልን አምላክ ብርታትና ጽናት እንዲሁም ምን ጊዜም የማይናወጥ የሕዝቡ አለኝታ መሠረት መሆኑን የሚያመ ለክት ነው:: 2ሳሙ22፥32፤ ዘዳ32፥4፡31፤ መዝ18፥31፤ኢሳ30፥29፤ 44፥8 ይመ::

2፥3 *በመታበይ አትናገሩ፤* የፍናናን፣ (የዔሊን ልጆች፣ የፍልስጥኤማውያንን፣ የሳዖልን፣ የናባልን፣ የጎልያድን፣ የአቤ ሴሎምን፣ የሳሚንና፣ የሳባን) ባሕርይ ያመለክታል:: *እግዚአብሔር*

የእስራኤላውያን እግር ከእንግዲህ ለቆ እንዲወጣ አላደርግም።” [9]ምናሴ ግን *እግዚአብሔር* በእስራኤላውያን ፊት ካጠፋቸው አሕዛብ የባሰ ክፉ ድርጊት ይፈጽሙ ዘንድ፣ የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን ሕዝብ አሳተ።

[10]*እግዚአብሔር* ለምናሴና ለሕዝቡ ተናገረ፤ እነርሱ ግን መስማት አልፈለጉም። [11]ስለዚህ *እግዚአብሔር* የአሦርን ንጉሥ ሰራዊት አዛዦች አመጣባቸው፤ እነርሱም በምናሴ አፍንጫ መንጠቆ አገቡበት፤ በናስ ሰንሰለት አስረውም ወደ ባቢሎን ወሰዱት። [12]በተጨነቀም ጊዜ *የአምላኩን* የእግዚአብሔርን በጎነት ፈለገ፤ በአባቶቹም አምላክ ፊት ራሱን እጅግ አዋረደ። [13]ወደ እርሱም በጸለየ ጊዜ፣ በጭንቀት ልመናውን ራርቶለት *እግዚአብሔር* ጸሎቱን ሰማው። ስለዚህ ወደ ኢየሩሳሌም፣ ወደ መንግሥቱም መለሰው፤ ምናሴም *እግዚአብሔር* አምላክ መሆኑን ዐወቀ።

[14]ከዚህ በኋላ በሸለቆው ውስጥ ከሚገኘው ከግዮን ምንጭ ምዕራብ አንሥቶ እስከ ዓሣ በር መግቢያ ድረስ ያለውን የዳዊትን ከተማ የውጭውን ቅጥር፣ የዖፌልን ኰረብታ እንዲከብብ በማድረግ፣ ይበልጥ ከፍ አድርጎ እንደ ገና ሠራው። በተመሸጉትም የይሁዳ ከተሞች ሁሉ የጦር አዛዦችን አኖረ።

[15]እንግዶች አማልክትንና ጣዖታቱን *ከእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ አስወገደ፤ በቤተ መቅደሱ ኰረብታና በኢየሩሳሌም የሠራቸውንም መሠዊያዎች ሁሉ አራቀ፤ ከከተማዪቱም ውጭ ጣላቸው። [16]ከዚያም *የእግዚአብሔርን* መሠዊያ አደሰ፤ በላዩም የኅብረት መሥዋዕትና የምስጋና መሥዋዕት አቀረበ፤ ይሁዳም *የእስራኤልን አምላክ* እግዚአብሔርን እንዲያገለግሉ አዘዘ። [17]ሕዝቡ ግን በኰረብታ መስገጃ ስፍራዎች መሠዋቱን ቢቀጥልም፣ የሚሠዋው ግን *ለአንዱ አምላክ* ለእግዚአብሔር ብቻ ነበር።

[18]በምናሴ ዘመነ መንግሥት የተከናወነው ሌላው ተግባር፣ ወደ አምላኩ ያቀረበው ጸሎቱና ባለራእዮች *በእስራኤል አምላክ* በእግዚአብሔር ስም የነገሩት ቃል በእስራኤል[ሀ] ነገሥታት ታሪክ ተጽፎአል። [19]ጸሎቱና እግዚአብሔር ራርቶ ልመናውን እንዴት እንደ ተቀበለው፣ ኀጢአቱ ሁሉና ታማኝነቱን ማጉደሉ፣ እንደዚሁም ራሱን ከማዋረዱ በፊት ያሠራቸው የኰረብታ መስገጃ ስፍራዎች፣ ያቆማቸው የአሼራ ምስል ዐምዶችና ጣዖታት ሁሉ በባለ ራእዮች መዛግብት ተጽፈዋል። [20]ምናሴም እንደ አባቶቹ ሁሉ አንቀላፋ፤ በቤተ መንግሥቱም ተቀበረ። ልጁም አሞጽ በእርሱ ፈንታ ነገሠ።

### የይሁዳ ንጉሥ አሞጽ

[21]አሞጽ በነገሠ ጊዜ ዕድሜው ሃያ ሁለት ዓመት ነበር፤ እርሱም በኢየሩሳሌም ተቀምጦ ሁለት ዓመት ገዛ። [22]አባቱ ምናሴ እንዳደረገው ሁሉ እርሱም *በእግዚአብሔር* ፊት ክፉ ድርጊት ፈጸመ፤ አሞጽም ምናሴ ያሠራቸውን ጣዖታት ሁሉ አመለከ፤ መሥዋዕትም አቀረበላቸው። [23]አሞጽ *በእግዚአብሔር* ፊት ራሱን እንዳዋረደ እንደ አባቱ እንደ ምናሴ ራሱን አላዋረደም፤ ነገር ግን በበደል ላይ በደል እየጨመረ ሄደ።

[24]የአሞጽ ሹማምንት በእርሱ ላይ አሢረው በቤተ መንግሥቱ ውስጥ ገደሉት። [25]ከዚያም ያገሩ ሕዝብ በንጉሡ አሞጽ ላይ ያሤሩትን ሁሉ ገደሉ፤ ልጁን ኢዮስያስንም በእርሱ ፈንታ አነገሡት።

[ሀ]18 በዜና መዋዕሉ መጽሐፍ ተደጋግሞ እንደተጠቀሰው ይህ ይሁዳ ነው።

33፥9 ዘሌ15፥4፤ ሕዝ5፥7
33፥11 ዘዳ28፥36፤ 2ነገ19፥28፤መዝ149፥8፤ኢሳ37፥29፤ሕዝ29፥4፤38፥4፤አሞ4፥2
33፥12 2ዜና6፥37
33፥14 1ነገ1፥33፤ 2ዜና27፥3፤ነህ3፥3፡26፤12፥39፤ሶፎ1፥10
33፥15 2ነገ23፥12
33፥16 ዘሌ7፥11-18
33፥19 2ነገ21፥2 1፥17፤2ዜና6፥37
33፥20 2ነገ21፥18፤ 2ዜና21፥20
33፥21 1ዜና3፥14
33፥23 ዘፀ10፥3፤ 2ዜና7፥14፤መዝ18፥27፤147፥6፤ምሳ3፥34
33፥25 2ዜና22፥1

*33፥10፤* የ1-20 ማብ ይመ። የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ እግዚአብሔር በነቢያቱ አማካይነት ለምናሴና እና ለሕዝቡ የተናገረውን እዚህ ላይ ባጭሩ አቅርቦታል፤ ሙሉ ታሪኩ በ2ነገ21፥10-15 ላይ ይገኛል።

*33፥11-17፤* በዜና መዋዕሉ ብቻ የሚገኝ ታሪክ ነው። ይህም ለሚታዘዙ በረከት ለማይታዘዙ የአጸፋ ቅጣት መኖሩን ለሚገልጸው ሐሳቡ አጽንዖት በመስጠት የምናሴ ክፋት ወረራና ሽንፈት እንዳመጣበት ሁሉ ንስሓ መግባቱ ደግሞ ወደ ሥልጣን እንዲመለስ እንደረዳው ያሳያል።

33፥11 *ወደ ባቢሎን ወሰዱት፤* እስካሁን ከቅዱሳት መጻሕፍት ውጭ ምናሴ በአሦር ንጉሥ ተማርኮ ወደ ባቢሎን ስለ መወሰዱ የሚናገሩ የታሪክ መዛግብት አልተገኙም፤ ከ681-669 ዓ.ቅ.ክ የነበረው አስራዶን ለሕንጻ ግንባታው ሥራ የተለያዩ ዕቃዎች ከሚያቀርቡለት ሃያ ሁለት ነገሥታት ውስጥ አንዱ ምናሴ መሆኑን ጠቅሶታል፤ ከ669-627 ዓ.ቅ.ክ. የነበረው አሹርባኒፓል ግብፅን በወረረ ጊዜ ከረዱት ነገሥታት መካከል አንዱ ምናሴ መሆኑን ገልጾአል፤ ይህ የአሦር ንጉሥ ምናሴን ማርኮ ወደ ባቢሎን የወሰደውም፣ የገዛ ወንድሙና የበታቹ ባለሥልጣን የነበረው ሽማሽ-ሹም-ዑኪን ዐምፆ በነበረበት ጊዜ ሳይሆን አይቀርም የሚል ግምት አለ። ዐመፁ የቈየው ለአራት ዓመት ያህል (652-648 ዓ.ቅ.ክ) ሲሆን፣ ምናልባትም ምናሴ የዐመፁ ተባባሪ ወይም ባቢሎን ከአሦር መንግሥት ለማፈንገጥ ባደረገው ሙከራ ተካፋይ ሳይሆን አይቀርም። ምናሴም ታማኝ ለመሆን እንደገና ቃል በመግባቱ፣ ይቅርታ ተደርጎለት ይሆናል፤ ወይም ጥፋት ያልተገኘበት ሆኖ ሊሆን ይችላል። ግብፅም በበኩሏ በሃያ ስድስተኛው ሥርወ መንግሥት ከአሦር እጅ አፈንግጣ ለመውጣት የተነሣችበት ጊዜ ስለ ነበር፣ ምናሴን መልሶ በዙፋኑ ላይ እንዲቀመጥ ማድረጉ አሦራውያን የሚያግዛቸውን ኀይል በግብፅ ወሰን ላይ የማስቀመጥ ፍላጎት እንደነበራቸው ያሳያል።

*33፥12፤* ቃልቶቹ የሰሎሞንን ጸሎት የሚያስታውስ ክፍል ነው (7፥14)።

33፥14 *የውጭውን ቅጥር... እንደገና ሠራው፤* ለዜና መዋዕሉ ጸሓፊ እንዲህ ያለው የግንባታ ሥራ በእግዚአብሔር የመባረክ ምልክት ነው (8፥1-6፤11፥5-12፤14፥6-7፤ 26፥9-10፡ 14-15፤32፥1-5፡27-30፤ 1ዜና፡11፥7-9፤15፥1)

*33፥15-16፤* ምናሴ ያመጣው ተሐድሶ ምን እንደ ሆነ በትክክል ባይታወቅም፣ ኢዮስያስ በኋለኛው ዘመን “ምናሴም በሁለት የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ አደባባዮች ላይ የሠራቸው መሠዊያዎች” እንዳፈረሰ ተጽፎአል (2ነገ23፥12)

33፥20 *በቤተ መንግሥቱም ተቀበረ፤* ከ2ነገ21፥18 ጋር ያነጻጽሩ። በዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ዘገባ መሠረት ምናሴ በቤተ መንግሥቱ ቅጥር ግቢ ውስጥ መቀበሩ፣ በነገሥታቱ መካነ መቃብር ካልተቀበሩት ነገሥታት መካከል አምስተኛው ንጉሥ ያደርገዋል (የ28፥27 ማብ ይመ)።

*33፥21-25፤* 2ነገ21፥19-26 ይመ፤ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ የዘገበው የአሞን ዘመነ መንግሥት ታሪክ (ከ642-640 ዓ.ቅ.ክ) በመጽሐፈ ነገሥት ከተጻፈው ጋር ፍጹም ተመሳሳይ ነው፤ የሚለይበት ነገር ቢኖር (1) አባቱ ምናሴ ንስሓ መግባቱንና ልጁ አሞን ግን ንስሓ አለመግባቱን ጨምሮ የገለጸው የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ብቻ መሆኑ ከቍ12-13፣ (2) ሥርዐተ ቀብሩ እንዴት እንደተፈጸመ አለመናገሩ ናቸው።

*34፥1-36፥1፤* 2ነገ22፥1-23፥30 እና ማብ ይመ። የኢዮሲያስን ዘመነ መንግሥት አስመልክቶ፣ ሁለቱም መጻሕፍት በተመሳሳይ መጠንና ዐይነት፣ በተመሳሳይ ርእሰ ጕዳይ ላይ ያተኰሩ ቢሆኑም እንኳ፣ በአጽንዖታቸው ግን በመጠኑ ይለያያሉ። ሁለቱም መጻሕፍ ኢዮስያስ ተሐድሶን ለማምጣት ያደረጋቸውን ሦስት መሠረታዊ ነገሮችን ዘርዝረዋል፤ እነዚህም (1) ባዕድ አምልኮን ማስወገድ፣ (2) የሕጉ መጽሐፍ መገኘትና ይህንን አስከትሎ የተደረገውን የኪዳን

## ኢዮስያስ ያደረገው ተሐድሶ

34፥1-2ተጓ ምብ —2ዜና22፥1-2
34፥3-7ተጓ ምብ —2ዜና23፥4-20
34፥8-13ተጓ ምብ —2ዜና22፥3-7

**34** ኢዮስያስ በነገሠ ጊዜ ዕድሜው ስምንት ዓመት ነበር፤ በኢየሩሳሌም ተቀምጦም ሠላሳ አንድ ዓመት ገዛ። [2]እርሱም በእግዚአብሔር ፊት መልካም የሆነውን ነገር አደረገ፤ ወደ ቀኝም ወደ ግራም ሳይል፣ በአባቱ በዳዊት መንገድ ሄደ።

[3]በዘመነ መንግሥቱ በስምንተኛው ዓመት ገና ወጣት ሳለ፣ የአባቱን የዳዊትን አምላክ መፈለግ ጀመረ፤ በዐሥራ ሁለተኛውም ዓመት ይሁዳንና ኢየሩሳሌምን ከኰረብታ መስገጃ ስፍራዎች፣ ከአሼራ፣ ምስል ዐምዶች፣ ከተቀረጹ ባዕዳትና ቀልጠው ከተሠሩ ምስሎች አነጻ። [4]በእርሱም ትእዛዝ የበአሊም መሠዊያዎችን አፈራረሱ፤ እርሱም ከበላያቸው የነበሩትን የዕጣን መሠዊያዎችን አደቀቀ፤ የአሼራን ምስል ዓምዶችን፣ ባዕዳቱንና ምስሎቹን ሰባብሮ ከፈጫቸው በኋላ ይሠዉ ላቸው በነበሩት ሰዎች መቃብር ላይ በተነ። [5]የካህናቱን ዐጥንት በመሠዊያዎቻቸው ላይ አቃጠለ፤ በዚህ ዐይነትም ይሁዳንና ኢየሩሳሌምን አነጻ። [6]እስከ ንፍታሌም ባሉ በምናሴ፣ በኤፍሬምና በስምዖን ከተሞች እንዲሁም በዙሪያቸው ባሉ የፈራረሱ አካባቢዎች፣ [7]መሠዊያዎችንና የአሼራ ምስል ዐምዶችን አፈራረሰ፤ ባዕዳቱን እንደ ዱቄት አደቀቀ፤ በመላው እስራኤል የሚገኙትንም የዕጣን መሠዊያዎች አነካከተ፤ ከዚያም ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሰ።

[8]ኢዮስያስ በነገሠ በዐሥራ ስምንተኛው ዓመት፣ ምድሪቱንና ቤተ መቅደሱን ካነጻ በኋላ፣ የኤዜልያስን ልጅ ሳፋንን፣ የከተማ ዪቱን ገዥ መዕሤያንና የጸሓፊውን የኢዮአካዝን ልጅ ኢዮአክን የአምላኩን የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ይጠግኑ ዘንድ ላካቸው።

[9]እነርሱም ወደ ሊቀ ካህኑ ወደ ኬልቅያስ ሄደው፣ ለእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ የመጣውን ገንዘብ ሰጡት፤ ገንዘቡም በር ጠባቂዎች የነበሩት ሌዋውያን፣ ከምናሴ፣ ከኤፍሬምና ከመላው የእስራኤል ቅሬታዎች እንደዚሁም ከመላው ይሁዳና ከብንያም፣ ከኢየሩሳሌምም ነዋሪዎች የሰበሰቡት ነበር። [10]እነርሱም የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ሥራ እየተቈጣጠሩ እንዲያሠሩ ለተሾሙት ሰዎች ዐደራ ሰጡ፤ እነዚህም ሰዎች ገንዘቡን ቤተ መቅደሱን ለጠገኑትና ላደሱት ሰዎች ከፈሉ። [11]እንዲሁም የይሁዳ ነገሥታት እንዲፈርሱ ላደረጓቸው ሕንጻዎች ጥርብ ድንጋዮችን፣ ሠረገላዎችንና ማገጣጠሚያ ዕንጨቶችን እንዲገዙ ለዐናጢዎችና ለግንበኞች ገንዘብ ሰጡ።

[12]ሰዎቹም ሥራውን በታማኝነት አከናወኑ። የበላይ ሆነው አመራር የሚሰጧቸውም ከሜራሪ ጐሣ የሆኑት ሌዋውያን፣ ኢኤትና አብድዩ፣ ከቀዓት ጐሣ ዘካርያስና ሜሱላም ነበሩ። በዜማ ዕቃ የላቀ ችሎታ የነበራቸው ሌዋውያን ሁሉ፣ [13]የጒልበት ሠራተኞች ኀላፊ በመሆን፣ በየሥራው ላይ የተመደቡትን ሠራተኞች ይቈጣጠሩ ነበር። ጥቂቶቹ ሌዋውያን ደግሞ ኀላፊዎች፣ ጸሓፊዎችና በር ጠባቂዎች ነበሩ።

34፥1 1ዜና3፥14፤ ሶፎ1፥1
34፥2 2ዜና29፥2
34፥3 1ዜና16፥11
34፥4 ዘፀ32፥20፤
34፥13፥ዘሌ26፥30፥2 ነገ23፥11፥ሚክ1፥5
34፥5 1ነገ13፥2
34፥7 ዘፀ32፥20
34፥9 1ዜና6፥13
34፥11 2ዜና24፥12፤33፥4-7
34፥12 2ነገ12፥15፤ 1ዜና25፥1
34፥13 1ዜና23፥4

## የሙሴ ሕግ መጽሐፍ መገኘት

34፥14-28ተጓ ምብ —2ዜና22፥8-20
34፥29-32ተጓ ምብ —2ዜና23፥1-3

[14]ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ የገባውን ገንዘብ በሚያወጡበት ጊዜ፣ ካህኑ ኬልቅያስ በሙሴ አማካይነት የተሰጠውን የእግዚአብሔርን ሕግ መጽሐፍ አገኘ። [15]ኬልቅያስም

---

መታደስ፣ (3) የፋሲካ በዓል መከበር ናቸው። በሁለተኛው ተራ ቍጥር ላይ የተጠቀሰውም ሐሳብ በተመለከተ ሁለቱም መጻሕፍት ተመሳሳይ የሆነ ዘገባ አቅርበዋል። በአንደኛው ተራ ቍጥር ላይ የተገለጸውን ሐሳብ በተመለከተ ግን የነገሥቱ ጸሓፊ በዝርዝር ሲጽፍ (2ነገ23፥4-20)፣ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ግን በአጭሩ አቅርቦታል 34፥3-7፡33። እንደዚሁም የፋሲካን በዓል በተመለከተ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ በዝርዝር ሲጽፍ (35፥1-19)፣ የነገሥቱ ጸሓፊ ግን ጠቀስ አድርጎት ብቻ አልፎአል (23፥21-23)። ታሪኩን አንዱ በዝርዝር፣ ሌላው ደግሞ በአጭሩ በመጻፉ ብቻ ሳይሆን፣ በቅደም ተከተልም ረገድ እንዲሁ ልዩነት አላቸው። በነገሥት መጽሐፍ ኢዮስያስ በነገሠ ዐሥራ ስምንተኛው ዓመት የሕጉ መጽሐፍ በቤተ መቅደስ የመገኘቱ ጒዳይ፣ ቅድሚያ ተሰጥቶት ተዘግቦአል። የነገሥቱ ጸሓፊ መልክዐ ምድራዊ ይዘት ባለው መንገድ መጀመሪያ ስለ ቤተ መቅደሱ፣ ቀጥሎም ስለ ከተማዪቱ ይጽፍና በመጨረሻም ስለተቀረው ሕዝብ ጽፎአል። በሌላ መልኩ ደግሞ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ዘገባውን ያቀረበው የድርጊቶችን ቅደም ተከተል በጠበቀ ሁኔታ ነው (34፥3 ፤ 34፥8፤ 2ነገ 22፥3 ፤35፥19፤2ነገ 23፥23 ይመ፤ እንዲሁም የ2ዜና 12፥2 ማብ ይመ)። የዜና መዋዕሉ መጽሐፍ ተሐድሶ የተጀመረው ኢዮስያስ በነገሠ በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት (34፥3) መሆኑን ዘግቦአል፣ ይህም የሕጉ መጽሐፍ ከመገኘቱ ከስድስት ዓመት በፊት ማለት ነው።

*34፥1-2፤* 2ነገ22፥1-2 ይመ።

*34፥1፤ ሠላሳ አንድ ዓመት፤* 640-609 ዓ.ክ.ት. ማለት ነው።

*34፥3-7፤* የነገሥቱ ጸሓፊ ይህን የኢዮስያስን ተሐድሶ በተመለከተ ያቀረበው ዘገባ፣ ሰፊና ዝርዝር ሁኔታዎችን የሚዳስስ ነው (2ነገ23፥4-20)። የባዕድ አምልኮ የመወገዱን ጒዳይ የዘገበው ስለ ሕጉ መጽሐፍ መገኘት ከዘገበ በኋላ ሲሆን፣ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ግን ቅድሚያ የሰጠው የባዕድ አምልኮ ስለመወገዱ ጒዳይ ነው።

*34፥3፤ አንዳንድ ሊቃውንት* በ8ኛው (ቍ3)፣በ12ኛው (ቍ3) ፣ በ18ኛው (ቍ8) የኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት የተፈጸሙትን ድርጊቶች፣ ለሁለት መቶ ዓመት በአካባቢው ሲገዛ ከቈየው፣ አሁን ግን ቀስ በቀስ ከተዳከመ በኋላ በወደቀው የአሦራውያን ግዛት ዐ ዌ ጋር ለማያያዝ ሞክረዋል። የአራምንና የፍልስጥኤምን ምድር ጠቅልሎ በቍጥጥሩ ሥር በማድረግ ለዘመናት ገኖ የነበረው የአሦር መንግሥት መውደቁ፣ ቀድሞ በይዞታው ሥር የነበሩትን አውራጃዎች እንደ ጥንቱ የዳዊትና የሰሎሞን ዘመን፣ ግዛቱ ለማ ድረግ ሁኔታዎችን ለኢዮስያስ ያመቻቸለት ለመሆኑ ጥርጥር የለውም (ቍ6-7)።

34፥6 *እስከ ንፍታሌም ባሉ በምናሴ፣ በኤፍሬምና በስምዖን፤* የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ "እስራኤል ሁሉ" ለሚለው ሐረግ ልዩ ትኩረት የሰጠው (በዜና መጽሐፍ መግቢያ ሥር፣ ዐበይት መሪ ሐሳብ' የሚለውን ይመ)፣ ኢዮስያስ ባደረገው ተሐድሶ የሰሜኑ ነገዶች ተካፋይ እንደነበሩ ለማመልከት ፈልጎ መሆኑ ግልጽ ነው ቍ9፡21፡33 ይመ)። የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ልክ በሕዝቅያስ ዘመን እንደ ሆነው እስራኤል ሁሉ በዳዊት ሥርወ መንግሥት ተጠቃ ለው አንድ እንደሆኑ ያሳያል (የ30፥1 ማብ ይመ)። *በስምዖን፤* ምናልባትም አንዳንድ የስምዖን ነገድ ሰዎች ከይሁዳ ወደ ሰሜኑ ክፍል ፈልሰው ሊሆን ይችላል።

34፥7 *በመላው እስራኤል፤* የነገድ ዝርዝራቸው በቍ6 ላይ ተገልጾአል።

*34፥8-21፤* 2ነገ 22፥3-13 እና ማብ ይመ።

34፥9 *ከምናሴ፣ ከኤፍሬምና ከመላው የእስራኤል ቅሬታዎች፤* የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ "እስራኤል ሁሉ" ለሚለው ሐረግ ከሚሰጠው ልዩ ትኵረት የተነሣ፣ እዚህም ላይ የሰሜኑ ክፍል ሰዎች ለቤተ መቅደሱ ስጦታ ማምጣታቸውን ዘግቦአል (ይህ ግን በ2ነገ22፥4 ላይ በግልጽ አልተጠቀሰም)።

*34፥10-13፤* ከ24፥8-12 ጋር ያነጻጽሩ።

*34፥22-28፤* 2ነገ22፥14-20 እና ማብ ይመ።

ጸሓፊውን ሳፋንን፣ "የሕጉን መጽሐፍ *በእግዚ አብሔር* ቤተ መቅደስ ውስጥ አገኘሁት" አለው፤ ከዚያም መጽሐፉን ለሳፋን ሰጠው።

[16]ሳፋንም መጽሐፉን ወደ ንጉሡ ወስዶ እንዲህ አለው፤ "ሹማምንትህ የታዘዙትን ሁሉ በመፈጸም ላይ ናቸው፤ [17]*በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ የነበረውንም ገንዘብ አውጥተው ለተቈጣጣሪዎቹና ለሠራተኞቹ አስረክበዋል።"

[18]ከዚያም ጸሓፊው ሳፋን ንጉሡን፣ "ካህኑ ኬልቅያስ መጽሐፍ ሰጥቶኛል" አለው። ሳፋንም መጽሐፉን ለንጉሡ አነበበለት።

[19]ንጉሡም የሕጉን ቃል በሰማ ጊዜ ልብሱን ቀደደ። [20]እርሱም ለኬልቅያስ፣ ለሳፋን ልጅ ለአኪቃም፣ ለሚክያስ ልጅ ለዓብዶን፣ ለጸሓፊው ለሳፋንና ለንጉሡ የቅርብ አገልጋይ ለዓሳያ ይህን ትእዛዝ ሰጠ፤ [21]"ሂዱና ስለ እኔ እንደዚሁም በእስራኤልና በይሁዳ ስላሉት ቅሬታዎች በተገኘው መጽሐፍ ውስጥ ስለ ተጻፈው ነገር *እግዚአብሔርን* ጠይቁ። አባቶቻችን *የእግዚአብሔርን* ቃል ስላልጠበቁ በላያችን ላይ ታላቅ *የእግዚአብሔርን* ቍጣ ፈስሶአል፤ በዚህ መጽሐፍ በተጻፈው መሠረት አልተመላለሱምና።"

[22]ኬልቅያስና ንጉሡ ከእርሱ ጋር የላካቸው[a] ሰዎች የአልባሳት ጠባቂ የነበረው የሐስራ ልጅ፣ የቲቁዋ ልጅ የሴሌም ሚስት ወደ ሆነችው ወደ ነቢይቱ ወደ ሕልዳና ሄደው ነገሯት። እርሷም በኢየሩሳሌም ውስጥ በሁለተኛው ክፍለ ከተማ ትኖር ነበር።

[23]ነቢይቱም እንዲህ አለቻቸው፤ "የእስራኤል *አምላክ* እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ወደ እኔ ለላካችሁ ሰው እንዲህ ብላችሁ ንገሩት፤ [24]'*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በይሁዳ ንጉሥ ፊት በተነበበው መጽሐፍ በተጻፈው ርግማን ሁሉ መሠረት፣ በዚህ ስፍራና በሕዝቡ ላይ ጥፋትን አመጣለሁ። [25]እኔን ትተውኝ ለሌሎች አማልክት ዕጣን ስላጠኑና እጃቸው በሠራው ነገር ሁሉ[b] ለቍጣ ስላነሣሡኝ፣ ቍጣዬ በዚህ ስፍራ ይነድዳል፤ አይጠፋምም።' [26]*እግዚአብሔርን* ለመጠየቅ የላካችሁን የይሁዳን ንጉሥ እንዲህ በሉት፤ 'ስለ ሰማኸው ቃል የእስራኤል አምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ [27]በዚህ ስፍራና በሕዝቡ ላይ የተናገረውን በሰማህ ጊዜ፣ ልብህ ስለ ተነካና በእግዚአብሔርም ፊት ራስህን ስለ አዋረድህ፣ እንዲሁም በእኔ ፊት ራስህን ዝቅ ስላደረግህ፣ ልብስህንም በመቅደድ በፊቴ ስለ አለቀስህ፣ ሰምቼሃለሁ ይላል *እግዚአብሔር*። [28]እነሆ፤ ወደ አባቶችህ እሰበስብሃለሁ፤ በሰላምም ትቀበራለህ፤ በዚህ ቦታና በነዋሪዎቹ ላይ የማመጣውን መከራ ሁሉ በዓይንህ አታይም።'" መልሷንም ይዘው ወደ ንጉሡ ሄዱ።

[29]ከዚያም ንጉሡ የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን ሽማግሌዎች ሁሉ በአንድ ላይ ሰበሰበ። [30]እርሱም ከትንሽ እስከ ትልቅ ካሉት ከይሁዳ ሰዎች፣ ከኢየሩሳሌም ሕዝብ፣ ከካህናትና ከሌዋውያን ጋር ወደ *እግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ወጣ። *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ የተገኘውንም የኪዳኑን መጽሐፍ ቃል ሁሉ ለሕዝቡ አነበበላቸው [31]ንጉሡም በዐምዱ አጠገብ ቆሞ፣ *እግዚአብሔርን* ይከተል ዘንድ በፍጹም ልቡና በፍጹም ነፍሱ ትእዛዛቱን፣ ሕግጋቱንና ሥርዐቱን ለመጠበቅ፣ በዚህ መጽሐፍ ለተጻፈውም የኪዳን ቃል ለመታዘዝ *በእግዚአብሔር* ፊት ኪዳኑን አደሰ።

[32]ከዚህ በኋላ በኢየሩሳሌምና በብንያም የሚኖረው ሁሉ በዚህ ነገር ቃል እንዲገባ አደረገ፤ የኢየሩሳሌምም ሕዝብ የአባቶቹ አምላክ ባዘዘው የአምላክ ቃል ኪዳን መሠረት ፈጸሙ።

[33]ኢዮስያስም አስጸያፊ ጣዖታትን ሁሉ ከመላው የእስራኤል ግዛት አስወገደ፤ በእስራኤል የነበሩትም ሁሉ አምላካቸውን *እግዚአብሔርን* እንዲያመልኩ አደረገ፤ እርሱ በሕይወት እያለም የአባቶቻቸውን *አምላክ* እግዚአብሔርን ከመከተል ወደ ኋላ አላሉም።

## ኢዮስያስ ፋሲካን ማክበሩ

35፥1፡18-19 ተጓ ምብ— 2ዜና 23፥21-23

**35** ኢዮስያስ በኢየሩሳሌም *ለእግዚአብሔር* ፋሲካን አደረገ፤ በመጀመሪያውም ወር በዐሥራ አራተኛው ቀን የፋሲካው በግ ታረደ። [2]ካህናቱን በየአገልግሎታቸው መደበ፤ *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ አገልግሎትም እንዲተጉ አበረታታቸው። [3]እስራኤልን ሁሉ ያስተምሩ ለነበሩትና ራሳቸውን *ለእግዚአብሔር* ለቀደሱት ሌዋውያን እንዲህ አላቸው፤ "የእግዚአብሔርን ታቦት የዳዊት ልጅ ሰሎሞን ባሠራው ቤተ መቅደስ አኑሩ፤ በእናንተ ትከሻ አትሸከሙት፤ አሁንም *አምላካችሁን* እግዚአብሔርንና ሕዝቡን እስራኤልን አገልግሉ። [4]በእስራኤል ንጉሥ በዳዊትና በልጁ በሰሎሞን በተጻፈው

[a]22 አንድ የዕብራይስጥ ቅጅ እንዲሁም ቩልጌትና የሱርስት ትርጕሞች በዚህ ሲስማሙ አብዛኞቹ የዕብራይስጥ ቅጆች ግን ከእርሱ ጋር የላካቸው የሚለውን አይጨምሩም።

[b]25 ወይም ባደረጉት ነገር ሁሉ

34፥15 2ነገ22፥8፤ ዕዝ7፥6፤ነህ8፥1
34፥19 ዘዳ28፥3-68፤ኢሳ36፥22፤37፥1
34፥20 2ነገ22፥3
34፥21 ሰቆ2፥4፤4፥11፤ሕዝ36፥18
34፥22 ዘፀ15፥20፤ነህ6፥14
34፥24 ዘዳ28፥15-68፤2ዜና36፥14-20፤ምሳ16፥4፤ኢሳ3፥9፤ኤር40፥2፤42፥10፤44፥2፡11
34፥25 2ዜና33፥3-6፤ኤር22፥9
34፥27 ዘፀ10፥3፤2ዜና6፥37፤32፥26
34፥28 2ዜና32፥26፤ 35፥20-35
34፥30 2ነገ23፥2
34፥31 ዘዳ13፥4፤1ነገ7፥15፤2ነገ11፥17፤2ዜና23፥16
34፥33 ዘዳ18፥9
35፥1 ዘፀ12፥1-30፤ዘኍ28፥16
35፥3 2ዜና17፥7
35፥4 ቍ10፤1ዜና24፥1፤ዕዝ6፥18

34፥28 *በሰላምም ትቀበራለህ፤* አሟሟቱንና ሥርዐተ ቀብሩን በተመለከተ 35፥20-25 *ይመ*።

*34፥29-31፤* 2ነገ23፥1-3 *ይመ*።

34፥30 *ከካህናትና ከሌዋውያን፤* "ካህናቱና ነቢያቱ" ከሚለው ከ2ነገ23፥2 *ጋር ያነጻጽሩ*።

34፥33 *ከመላው እስራኤል ግዛት.. በእስራኤል የነበሩትም ሁሉ፤* የቍ6 *ማብ ይመ*።

*35፥1-19፤* ኢዮስያስ የፋሲካን በዓል እንዴት እንዳከበረ በመጽሐፈ ነገሥት ላይ ባጭሩ ከቀረበው ይልቅ (2ነገ23፥21-23) የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ በዝርዝር ጽፎአል።

35፥1 *በመጀመሪያውም ወር፤* የፋሲካ በዓል የሚከበርበት ወር ነው፤ ከሕዝቅያስ የፋሲካ በዓል አከባበር *ጋር ያነጻጽሩ* (የ30፥2 *ማብ ይመ*)።

35፥3 *የእግዚአብሔርን ታቦት ... በቤተ መቅደስ አኑሩ።* ቀድሞውኑ ታቦቱ ለምን ከዚያ እንደወጣ የሚገልጽ ጽሑፍ በነገሥቱም ሆነ በዜና መዋዕሉ መጽሐፍ ተጽፎ አይገኝም፤ ምናልባት ከኢዮስያስ በፊት በነበሩት በክፉዎቹ ነገሥታት በምናሴና በአሞጽ ዘመነ መንግሥት፣ ለጥንቃቄ ሲባል ወደ ሌላ ቦታ ሳያዛውሩት እንዳልቀረ ይገመታል።

35፥4 *በዳዊትና ...በሰሎሞን፤* የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ዳዊትንና ሰሎሞንን በሦስት ነገሮች ያመሳስላቸዋል፤ (1) 7፥10 (ዳዊት ብቻ ከተጠቀሰበት ከ1ነገ 8-66 *ጋር ያነጻጽሩ*)፤ (2) 11፥17 እና (3) እዚሁ ላይ ነው፤ ጸሓፊው የፈለገው ለዳዊትና ለሰሎሞን ያለውን ከፍተኛ አክብሮትና አድናቆት ለመግለጽ ነው (የ1ዜናን መግቢያ የዳዊትና

መመሪያ መሠረት፣ እንደየቤተሰባችሁ በክፍል በክፍላችሁ ራሳችሁን አዘጋጁ።

[5]“ሌዋውያን ባልሆኑ ወንድሞቻችሁ አንጻር እንደየቤተሰቡ ምድብ በተቀደሰው ስፍራ ቁሙ፤ ለእያንዳንዱም የቤተሰብ ምድብ ሌዋውያን ይኑሩት። [6]ከዚያም የፋሲካውን በጎች እረዱ፤ ራሳችሁን ቀድሱ፤ እግዚአብሔር በሙሴ አማካይነት ባዘዘውም መሠረት ዕርዶቹን ለወንድሞቻችሁ አዘጋጁ።”

[7]ኢዮስያስም እዚያ ለነበሩት ሕዝብ ሁሉ ለፋሲካው መሥዋዕት እንዲሆኑ ባጠቃላይ ሠላሳ ሺህ በግና ፍየል እንዲሁም ሦስት ሺህ ወይፈን ከራሱ ሃብት ሰጠ።

[8]ሹማምንቱም ለሕዝቡ፣ ለካህናቱና ለሌዋውያኑ በገዛ ፈቃዳቸው አዋጥተው ሰጡ። የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ አለቆች የሆኑት ኬልቅያስ፣ ዘካርያስና ይሒኤልም ለፋሲካ መሥዋዕት የሚቀርቡ ሁለት ሺህ ስድስት መቶ በግ እንዲሁም ሦስት መቶ ወይፈን ሰጡ። [9]ደግሞም ኮናንያ፣ ወንድሞቹ ሸማያና ናትናኤል እንደዚሁም የሌዋውያኑ መሪዎች ሐሸቢያ፣ ይዒኤልና ዮዛባት ለፋሲካ መሥዋዕት እንዲሆኑ አምስት ሺህ በግና ፍየል አምስት መቶም በሬ ለሌዋውያኑ ሰጧቸው።

[10]የአገልግሎቱ ዝግጅት በተጠናቀቀ ጊዜ፣ ንጉሡ ባዘዘው መሠረት ካህናቱ በየክፍላቸው ከተመደቡት ሌዋውያን ጋር ቦታ ቦታቸውን ይዘው ቆሙ። [11]የፋሲካው በጎች ታረዱ፤ ካህናቱ የተቀበሉትን ደም ረጩ፤ ሌዋውያኑም የበጎቹን ቈዳ ገፈፉ። [12]በሙሴ ሕግ እንደ ተጻፈው ለእግዚአብሔር እንዲያቀርቡም፣ እንደ የቤተሰቡና እንደየምድቡ ለሕዝቡ ለመስጠት የሚቃጠለውን መሥዋዕት ለዩ፤ ወይፈኖቹንም እንደዚሁ አደረጉ። [13]እነርሱም የፋሲካውን መሥዋዕት በሥርዐቱ መሠረት ጠበሱ፤ የተቀደሰውንም ቍርባን በምንቸት፣ በሰታቴና በድስት ቀቀሉ፤ ወዲያውኑም ለሕዝቡ አደሉ። [14]ከዚህ በኋላ ለራሳቸውና ለካህናቱ ዝግጅት አደረጉ፤ ምክንያቱም ካህናቱ የአሮን ልጆች የሚቃጠለውን መሥዋዕትና ስቡን እስከ ሌሊት ድረስ ያቀርቡ ስለ ነበር ነው። ስለዚህ ሌዋውያኑ ለራሳቸውና ለካህናቱ ለአሮን ልጆች ዝግጅት አደረጉ።

[15]መዘምራኑ የአሳፍ ዘሮች በዳዊት፣ በአሳፍ፣ በኤማንና በንጉሡ ባለ ራእይ በኤዶታም በተሰጠው መመሪያ መሠረት በቦታቸው ነበሩ። በእያንዳንዱ በር ላይ የነበሩት በር ጠባቂዎችም ሌዋውያን ወገኖቻቸው ስላዘጋጁላቸው፣ ከጥበቃ ቦታቸው መለየት አያስፈልጋቸውም ነበር።

[16]በዚህ ዓይነት የፋሲካን በዓል በማክበርና የሚቃጠል መሥዋዕት በእግዚአብሔር መሠዊያ ላይ በማቅረብ የእግዚአብሔር አግልግሎት ሁሉ ንጉሥ ኢዮስያስ ባዘዘው መሠረት በዚያኑ ቀን ተከናወነ። [17]በዚያን ጊዜ በስፍራው የተገኙ እስራኤላውያን የፋሲካን በዓል አከበሩ፤ የቂጣንም በዓል እንደዚሁ ሰባት ቀን አከበሩ። [18]ከነቢዩ ከሳሙኤል ዘመን ወዲህ እንዲህ ያለ ፋሲካ በእስራኤል ዘንድ ተከብሮ አያውቅም፤ ኢዮስያስ ከካህናቱ፣ ከሌዋውያኑ፣ ከመላው ይሁዳና ከእስራኤል፣ በዚያ ከነበሩትም ከኢየሩሳሌም ሰዎች ጋር እንዳከበረው አድርጎ ያከበረ አንድም የእስራኤል ንጉሥ የለም። [19]ይህ ፋሲካ የተከበረው በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት በዐሥራ ስምንተኛው ዓመት ነበር።

### የኢዮስያስ መሞት

35፥20-36፥1 ተጓ ምብ —2ዜና23፥28-30

[20]ከዚህ ሁሉ በኋላ ኢዮስያስ ቤተ መቅደሱን አደራጅቶ ባጠናቀቀ ጊዜ፣ የግብፅ ንጉሥ ኒካዑ በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ፣ በከርከሚሽ ላይ ለመዋጋት ወጣ፤ ኢዮስያስም ጦርነት ሊገጥመው ወጣ። [21]ኒካዑ ግን፣ “የይሁዳ ንጉሥ ሆይ፤ አንተንና እኔን የሚያጣላን ምንድነው? ጦርነት ከገጠምሁት ቤት ጋር እንጂ በአሁኑ ጊዜ አንተን የምወጋህ አይደለሁም፤ እግዚአብሔር እንድፈጥን አዞኛል፤ ስለዚህ ከእኔ ጋር ያለውን እግዚአብሔርን መቃወምህን ተው፤ ያለዚያ ያጠፋሃል” አለው።

[22]ኢዮስያስ ግን ሌላ ሰው መስሎ በጦርነት ሊገጥመው ወጣ እንጂ ወደ ኋላ አልተመለሰም፤ በመጊዶ ሜዳ ላይ ሊዋጋው ሄደ እንጂ ኒካዑ ከእግዚአብሔር ታዞ የነገረውን ሊሰማ አልፈለገም።

[23]ቀስተኞች ንጉሥ ኢዮስያስን ወጉት፤ እርሱም የጦር መኰንኖቹን፣ “ክፉኛ ቈስያለሁና ከዚህ አውጡኝ” አላቸው። [24]ስለዚህ ከሠረገላው አውርደው በራሱ ሠረገላ ላይ አስቀምጠውት

35፥6 ዘሌ11፥44
35፥7 2ዜና30፥24፤ 31፥3
35፥8 1ዜና6፥13፤ 29፥3፤2ዜና29፥31-36
35፥9 2ዜና31፥12፡ 13
35፥10 ቊ4፤ 2ዜና30፥16
35፥11 2ዜና30፥17
35፥13 ዘፀ12፥2-11
35፥14 ዘፀ29፥13
35፥15 1ዜና25፥1፤ 26፥12-19፤2ዜና2 9፥30፤ነህ1 2፥46፤መዝ6 8፥25
35፥20 ዘፍ2፥14፤ ኢሳ10፥9፤ኤር46፥2
35፥21 1ነገ13፥18፤ 2ነገ18፥25
35፥22 1ሳሙ28፥8
35፥23 1ነገ22፥34

የሰሎሞን ገጸ ባሕርይ አሣሣል የሚለውን ይመ)።

*35፥7-9፤* በዜና መዋዕሉ መጽሐፍት በፈቃደኝነትና በደስታ መስጠት ትልቅ ትኵረት ተሰጥቶታል (24፥8-14፤ 29፥31-36፤ 31፥3-21፤ 1ዜና29፥3-9)፤ ይህም በድኅረ ምርኮ ለነበሩት ለመጽሐፉ ተደራሲያን ትልቅ ጠቀሜታ እንደ ነበረው ይገመታል።

35፥18 ***ከነቢዩ ከሳሙኤል ዘመን ወዲህ*** በመጽሐፈ ነገሥት የተጻፈው ግን፣ “ከመሳፍንት ዘመን ጀምሮ” (2ነገ23፥22) ተብሎ ነው ።

35፥19 ***በዐሥራ ስምንተኛው ዓመት፤*** የሕጉ መጽሐፍ ከተገኘበት ዓመት ጋር አንድ ነው (34፥8፡14)።

*35፥20-27፤* 2ነገ23፥28-30 ይመ። በ609 ዓ.ቅ.ክ ላይ “የግብፅ ንጉሥ ፈርዖን ኒካዑ” ከባቢሎናውያን ጋር ለመዋጋት፣ “የአሦርን ንጉሥ ለመርዳት ወደ ኤፍራጥስ ወንዝ ወጥቶ ነበር” (2ነገ 23-29)።

35፥20፤ ***በከርከሚሽ፤*** ይህ ቦታ በመጽሐፈ ነገሥት ላይ አልተጠቀሰም።

*35፥21-22፤* በዜና መዋዕሉ ላይ ብቻ ተጽፎ የሚገኝ ነው፤ ይኸውም ቢታዘዙ በረከት ባይታዘዙ ደግሞ ቅጣት መኖሩን ለማሳየት ጸሐፊው ደጋግሞ የሚያሳየው ጒዳይ ነው። ኢዮስያስ በጦርነቱ ሊገደል የቻለው፣ ፈርዖን ምንም እንኳን አሕዛብ ቢሆንም በእርሱ አፍ የተናገረውን የእግዚአብሔርን ቃል ስላልታዘዘው ነው።

35፥21 ***ጦርነት ከገጠምሁት ቤት ጋር፤*** ከባቢሎናውያን ጋር ማለት ነው። በጊዜው በዙፋን ላይ የነበረው ንጉሥ ናቦፖላሳር ሲሆን፣ በጦርነቱ ላይ ሰራዊቱን ይመራ የነበረው ግን ልጁ ናቡከደነፆር ነበር። 605 ዓ.ቅ.ክ ላይ በከርከሚሽ ከግብፅ ጋር ከተደረገው ሌላ ጦርነት በኋላ፣ ናቡከደናፆር በአባቱ እግር ተተካ። ምናልባት ኢዮስያስ ሊረዳው የመጣው የባቢሎንን ንጉሥ ሳይሆን አይቀርም 32፥31፤33፥11 እና ማብ ይመ)።

35፥22 ***ሌላ ሰው መስሎ፤*** ከአክአብና ከኢዮሣፍጥ ጋር ያነጻጽሩ (18፥29 እና ማብ ይመ)። ***በመጊዶ ሜዳ፤*** የመሳ. 5፥19 ማብ ይመ።

*35፥24-25፤* በዜና መዋዕሉ ላይ ብቻ ተጽፎ የሚገኝ ነው።

35፥25 ***ኤርምያስ ለኢዮስያስ የሐዘን ግጥም ጻፈለት፤***

ወደ ኢየሩሳሌም ወሰዱት፤ እዚያም ሞተ፤ በአባቶቹ መካነ መቃብር ተቀበረ፤ የይሁዳና የኢየሩሳሌም ሕዝብ ሁሉ አለቀሱለት።

[25]ኤርምያስ ለኢዮስያስ የሐዘን እንጕርጕሮ ግጥም ጻፈለት፤ ወንዶችና ሴቶች ሙሾ አውራጆች ሁሉ እስከ ዛሬ ድረስ በዚህ ግጥም ኢዮስያስን ያስታውሱታል፤ ይህም በእስራኤል የተለመደ ሆኖ በልቅሶ ግጥም መጽሐፍ ተጽፎአል።

[26]በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት የተከናወነው ሌላው ድርጊትና *በእግዚአብሔር* የሕግ መጽሐፍ በተጻፈው መሠረት ያከናወነው መንፈሳዊ ተግባር፣ [27]ከመጀመሪያው እስከ መጨረሻው ያደረገው ሁሉ በይሁዳና በእስራኤል ነገሥታት መጽሐፍ ተጽፎአል።

**36** የአገሩም ሰዎች የኢዮስያስን ልጅ ኢዮአሐዝን ወስደው በአባቱ ፈንታ በኢየሩሳሌም አነገሡት።

## የይሁዳ ንጉሥ ኢዮአሐዝ

36፥2-4ተን ምብ —2ዜና23፥31-34

[2]ኢዮአሐዝ በነገሠ ጊዜ፣ ዕድሜው ሃያ ሦስት ዓመት ነበር፤ በኢየሩሳሌም ተቀምጦም ሦስት ወር ገዛ። [3]ከዚያም የግብፅ ንጉሥ በኢየሩሳሌም ካለው ዙፋኑ አወረደው፣ በአገሩም ላይ አንድ መቶ መክሊት[a] ብርና አንድ መክሊት[b] ወርቅ ግብር ጣለበት። [4]የግብፅም ንጉሥ የኢዮአሐዝን ወንድም ኤልያቄምን በይሁዳና በኢየሩሳሌም ላይ አነገሠው፤ ስሙንም ለውጦ ኢዮአቄም አለው። ኒካዑም የኤልያቄምን ወንድም ኢዮአሐዝን ይዞ ወደ ግብፅ ወሰደው።

## የይሁዳ ንጉሥ ኢዮአቄም

36፥5-8ተን ምብ —2ዜና23፥36-24፥6

[5]ኢዮአቄም በነገሠ ጊዜ፣ ዕድሜው ሃያ አምስት ዓመት ነበር፤ በኢየሩሳሌም ተቀምጦም ዐሥራ አንድ ዓመት ገዛ። *በአምላኩም በእግዚአብሔር* ፊት ክፉ ድርጊት ፈጸመ። [6]የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በእርሱ ላይ ዘመተ፤ ወደ ባቢሎንም ይወስደው ዘንድ በናስ ሰንሰለት አሰረው። [7]እንደዚሁም ናቡ ከደነፆር *የእግዚአብሔርን* ቤተ መቅደስ ዕቃ ወስዶ፣ ባቢሎን ባለው በራሱ ቤተ ጣዖት[c] አኖረው።

[8]በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት የተከናወነው ሌላው ተግባሩ የፈጸመው አስጸያፊ ድርጊትና በእርሱ ላይ የተገኘበት ሁሉ በእስራኤልና በይሁዳ ነገሥታት መጽሐፍ ተጽፎአል። ልጁ ዮአኪንም በእርሱ ፈንታ ነገሠ።

## የይሁዳ ንጉሥ ዮአኪን

36፥9-10ተን ምብ —2ዜና24፥8-17

[9]ዮአኪን በነገሠ ጊዜ፣ ዕድሜው ዐሥራ ስምንት[d] ዓመት ነበር፤ በኢየሩሳሌም ተቀምጦም ሦስት ወር ከዐሥር ቀን ገዛ፤ እርሱም *በእግዚአብሔር* ፊት ክፉ ድርጊት ፈጸመ። [10]በጸደይም ወራት ንጉሡ ናቡከደነፆር ልኮ *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ውስጥ ከፍተኛ ዋጋ ካላቸው ዕቃዎች ጋር ወደ ባቢሎን ወሰደው። የዮአኪንንም አጎት[e] ሴዴቅያስን በይሁዳና በኢየሩሳሌም ላይ አነገሠው።

## የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ

36፥11-16ተን ምብ—2ዜና24፥18፤ኤር52፥1-3

[11]ሴዴቅያስ በነገሠ ጊዜ፣ ዕድሜው ሃያ አንድ ዓመት ነበር፤ በኢየሩሳሌም ተቀምጦም ዐሥራ አንድ ዓመት ገዛ። [12]እርሱም በአምላኩ *በእግዚአብሔር* ፊት ክፉ ድርጊት ፈጸመ፤ የእግዚአብሔርን ቃል በተናገረው በነቢዩ በኤርምያስ ፊትም ራሱን ዝቅ አላደረገም። [13]እንደዚሁም በእግዚአብሔር ስም አምሎት በነበረው በንጉሥ ናቡከደነፆር ላይ ዐመፀ፤ አንገቱን አደነደነ፤ ልቡንም አጠነከረ እንጂ ወደ እስራኤል ስምላክ ወደ *እግዚአብሔር* አልተመለሰም። [14]ከዚህም በላይ የካህናቱና የሕዝቡ መሪዎች ሁሉ፣ አስጸያፊ የሆኑትን የአሕዛብን ልማዶች በመከተልና በኢየሩሳሌም የተቀደሰውን *እግዚአብሔርን* ቤተ መቅደስ

[a]3 3.4 ሜትሪክ ቶን ያህል ነው።
[b]3 34 ኪሎ ግራም ይሆል ነው።
[c]7 ወይም *ቤተ መንግሥት* ተብሎ መተርጐም ይቻላል።
[d]9 አንድ የዕብራይስጥ ቅጂ ጥቂት የሰብዓ ሊቃናትና የሱርስት ትርጕሞች (እንዲሁም 2ነገ24፥8) ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ ብዙ የዕብራይስጥ ቅጆች ግን *ስምንት* ይላሉ።
[e]10 ዕብራይስጡ *ወንድም* ይላል (እንዲሁም 2ነገ24፥17 ይመ)።

35፥25 ዘፍ50፥10፤ 2ዜና34፥28፤ኤር22፥10፡15፡16
36፥1 2ዜና22፥1
36፥4 ኤር22፥10-12፤ሕዝ19፥4
36፥5 ኤር22፥18፤ 25፥1፤26፥1፤35፥1፤36፥1፤45፥1፤46፥2
36፥6 ኤር25፥9፤ 27፥6፤ሕዝ19፥9፤ 29፥18፤ዳን1፥1
36፥7 ቍ18፤ዕዝ 1፥7፤ ኤር27፥16፤ ዳን1፥2
36፥9 ኤር22፥24-28፤24፥1፤27፥20፤29፥2፤52፥31
36፥10 ቍ18፤ 2ነገ20፥17፤ ዕዝ1፥7፤ኢሳ52፥11፤ ኤር14፥18፤21፥7፤22፥25፤24፥1፤ 27፥16፡20፡22፤29፥1፤34፥21፤40፥1፤ሕዝ17፥12፤ዳን5፥2
36፥11 2ነገ24፥17፤ ኤር27፥1፤28፥1፤34፥2፤37፥1፤39፥1
36፥12 ዘዳ8፥3፤ 2ዜና7፥14፤ኤር37፥1፤39፥18፤44፥10
36፥13 ዘዳ32፥9፤ ዘዳ9፥27፤ሕዝ17፥13
36፥14 1ዜና5፥25

ኤርምያስ ኢዮስያስን የሚመለከተው እጅግ ከፍ ባለ አክብሮት ነበር (ኤር22፥15-16)። የጻፈለት የሐዘን እንጕርጕሮ አሁን አይገኝም። የሰቆቃውን መጽሐፍ የጻፈው ኤርምያስ ነው ተብሎ በትውፊት የሚነገረው ከዚህ የተነሣ ነው። *እስከ ዛሬ ድረስ፤* የ5፥9 ማብ ይመ ።

*36፥2-14፤* ከእርሱ በኋላ በተከታታይ ሦስት ልጆቹ የነገሡለት የይሁዳ ንጉሥ ኢዮስያስ ብቻ ነው (ኢዮአሐዝ፣ ኢዮአቄም፣ ሴዴቅያስ)። የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ስለተቀሩት የይሁዳ ነገሥታት ታሪክ የጻፈው አሳጥሮ ነው።

*36፥2፤* 2ነገ23፥31-35 ይመ። ኢዮስያስ በፈርዖን ኒካዑ እጅ ከተገደለ በኋላ፣ የይሁዳ ምድር ለተወሰነ ጊዜ በግብፅ አገዛዝ ሥር ወድቃለች (ቍ3-4)። *ሦስት ወር፤* 609 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው። ኒካዑ ሥልጣኑን አደላድሎ ይሁዳን በቍጥጥሩ ሥር ሲያደርግ በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት ሰፍኖ የነበረው የሃያ ዓመት ነጻነት አከተመ። ይህን አጭር የአገዛዝ ዘመን አስመልክቶ የዜና መዋዕሉ ጸሓፊ ምንም ዐይነት ግብረገባዊ ፍርድ አልሰጠም፤ ነገር ግን የነገሥቱ ጸሓፊ ስለዚህ ነገር ብዙ ብሎአል (2ነገ23፥32)።

*36፥4፤* ኒካዑ ኢዮአሐዝን ወደ ምርኮ በመውሰድ፣ ለኤልያቄም ኢዮአቄም ብሎ ስም በማውጣት እንዳነገሠው ሁሉ፣ ናቡከደነፆር ኢዮአቄምን ወደ ባቢሎን በምርኮ በመውሰድ ለሴዴቅያስ ማታንያን የሚል ስም በመስጠት በምትኩ አንግሦታል (2ነገ24፥15-17)። ድል አድራጊዎቹ ግብፅና ባቢሎን የየራሳቸውን ሰዎች በዙፋን ላይ አስቀምጠዋል፤ የስም ለውጡም ባስቀመጡት ሰው ላይ ሥልጣን እንዳላቸው የሚያመለክት ነው።

*36፥5-8፤* 2ነገ23፥36-24፥7 ይመ። ኢዮአቄም ነቢያትን ያሠቃየ ንጉሥ ስለ ነበር፣ ኤርምያስ በከፍተኛ ሁኔታ አውግዞታል (ኤር 25-26፤36)። በ605 ዓ.ቅ.ክ. ላይ ግብፅ በከርከሚሽ ድል ስትደረግ (ኤር46፥2)፣ ኢዮአቄም ከባቢሎን ንጉሥ ከናቡከደነፆር ጋር ኅብረትን ፈጠረ። በኋላ ደግሞ ከባቢሎን ጋር የነበረውን ኅብረት በማቋረጥ ከግብፅ ንጉሥ ጋር በማበሩ የባቢሎን ንጉሥ የበቀል ቅጣት የሚወስዱ ሰራዊት ሰደደበት። ይሁን እንጂ ይህ ሰራዊት ገና እዚያ ከመድረሱ በፊት ኢዮአቄም ሞተ፤ ስለዚህም ልጁን ዮአኪንን ምርኮኛ በማድረግ ወደ ባቢሎን ወሰዱት።

36፥5 *ዐሥራ አንድ ዓመት፤* 609-598 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው።

*36፥9-10፤* 2ነገ24፥8-17፤ እንዲሁም ኤር22፥24-28፤24፥1፤29፥2፤52፥31 ይመ። ምንም እንኳ ዮአኪን ንግሥት ከሆነችው ከእናቱና ከሹማምንቱ እንዲሁም ከብዙ ሕዝብ ጋር ቢወሰድም (597 ዓ.ቅ.ክ)፣ በምትኩ ሴዴቅያስ ነግሦአል፤ በሴዴቅያስም የንግሥና ዘመን ሁሉ ዮአኪን ምርኮኛ ነበር (ኤር52፥31፤ ሕዝ 1፥2፤ እንዲሁም ከኢስ.2፥5-6 ጋር ያነጻጽሩ)።

36፥9 *ሦስት ወር ከዐሥር ቀን፤* 598-597 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው።

*36፥11-14፤* 2ነገ 24፥18-20፤ ኤር 52፥1-3 ይመ፤ ከቍ 13-14 ያለው ክፍል በዚህ መጽሐፍ ላይ ብቻ የሚገኝ ነው (ከኤር 1፥3፤ 21፥1-7፤ 24፥8፤27፥1-15፤ 32፥1-5፤34፥1-7፡21፤37፥1-39፥7 ጋር ያነጻ

በማርከስ፣ ባለመታመናቸው ከጊዜ ወደ ጊዜ እየባሱ ሄዱ።

## የኢየሩሳሌም መውደቅ

36፥17-20፥ተጓ ምብ —2ዜና25፥1-21፤ኤር52፥4-7
36፥22-23 ተጓ ምብ — ዕዝራ1፥1-3

[15]የአባቶቻቸው *አምላክ* እግዚአብሔር ለሕዝቡና ለማደሪያው ስላዘነ፣ መልእክተኞቹን ይልክ ነበር፤ [16]እነርሱ ግን የእግዚአብሔር ቍጣ በሕዝቡ ላይ እስኪነሣና ፈውስም እስከማይገኝላቸው ድረስ በእግዚአብሔር መልእክተኞች ላይ ተሳለቁ፤ ቃሉን ናቁ፤ ነቢያቱንም አቃለሉ። [17]ስለዚህ የባቢሎናውያንን ንጉሥ አመጣባቸው፤ እርሱም ወጣቶቻቸውን በቤተ መቅደሱ ውስጥ በሰይፍ ፈጀ፤ ወጣቱንም ሆነ ወጣቲቱን፣ ሽማግሌውንም ሆነ በዕድሜ የገፋውን አላስ ቀረም፤ እግዚአብሔር ሁሉንም ለናቡከደናፆር አሳልፎ ሰጠው። [18]እርሱም ትልልቁንም ሆነ ትንንሹን የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ዕቃ በሙሉ፣ እንዲሁም የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ሀብት፣ የንጉሡንና የሹማምንቱን ሀብት ሁሉ ወደ ባቢሎን አጋዘ። [19]የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ በእሳት አቃጠሉ፤ የኢየሩ ሳሌምን ቅጥሮች አፈረሱ፤ ቤተ መንግሥ ቶቹን በሙሉ አቃጠሉ፤ በዚያ የነበረውንም የከበረ ዕቃ በሙሉ አጠፉ።

[20]ከሰይፍ የተረፉትን ቅሬታዎች በምርኮ ወደ ባቢሎን ወሰዳቸው፤ እስከ ፋርስ መንግሥት መነሣትም ድረስ የእርሱና የልጆቹ አገልጋዮች ሆኑ። [21]ምድሪቱም የሰንበት ዕረፍት አገኘች፤ በኤርምያስ የተነገረው *የእግዚአብሔር* ቃል ይፈጸም ዘንድ፣ ሰባው ዓመት እስኪያበቃ ድረስ፣ ባድማ በነበረችበት ዘመን ሁሉ ዐረፈች።

[22]በኤርምያስ የተነገረው *የእግዚአብሔር* ቃል ይፈጸም ዘንድ፣ በፋርስ ንጉሥ በቂሮስ ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ዓመት፣ በግዛቱ ሁሉ ዐዋጅ እንዲያስነግርና ይህም እንዲጻፍ *እግዚአብሔር* የፋርስን ንጉሥ የቂሮስን መንፈስ አነሣሣ፤ እርሱም እንዲህ አለ፤

[23] "የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ እንዲህ ይላል፤" 'የሰማይ *አምላክ* እግዚአብሔር የም ድርን መንግሥታት ሁሉ ሰጥቶኛል፤ በይሁዳ በምትገኘው በኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ እሠራለት ዘንድ አዝዞኛል፤ ከሕዝቡ በመ ካከላችሁ የሚገኝ ማናቸውም ሰው፣ *እግዚአብሔር* አምላኩ ከእርሱ ጋር ይሁን፤ እርሱም ወደዚያው ይውጣ።' "

36፥15 ኢሳ5፥4፤ 44፥26፤ኤር7፥13፡25፤11፥7፤25፥3-4፤ 35፥14፡15፤44፥4-6 ሐጌ1፥13፤ዘካ1፥4፤ ሚል2፥7፤3፥1፤ ማቴ5፥12
36፥16 2ነገ2፥23፤ ዕዝ5፥12፤ነህ9፥30፤ ኢዮ8፥2፤ምሳ1፥30-31፤29፥1፤ ኢሳ28፥14፡ 22፤ 29፥20፤57፥4፤ ኤር5፥13፤7፥26፤ 20፥8፤25፥4፤30፥12፤ 43፥2፤44፥3፤ዳን9፥6፤ ሚክ2፥11፤ዘካ1፥2
36፥17 ዘፍ10፥10፤ ዘዳ32፥25፤ዕዝ5፥12፤ኤር6፥11፤9፥21፤ 18፥21፤32፥28፤ 44፥7፤ 51፥22፤ ሰቆ2፥21፤ ሕዝ9፥6፤23፥47
36፥18 ቍ7፡10፤ ኤር27፥20
36፥19 1ነገ9፥8-9፤2ነገ14፥13፤መዝ79፥1-3፤ ኤር11፥16፤17፥27፤ 21፥10፤14፤22፥7፤32፥29፤39፥8፤ ሰቆ2፥6፤4፥11፤ ሕዝ20፥47፤አሞ
36፥20 ዘሌ26፥44፤ 2ነገ24፥14፤ዕዝ2፥1፤ ነህ7፥6፤ኤር27፥7
36፥21 ዘሌ25፥4፤ 1ዜና22፥9፤ ኤር1፥1፤ 25፥11፤ 27፥22፤ 29፥10፤ 40፥1፤ዳን9፥2፤ዘካ1፥12፤7፥5 36፥22 ኢሳ44፥28፤ 45፥1፡13፤ዳን1፥21፤6፥28፤10፥1

[a]17 ወይም *ከለዳውያን*

ጽሩ)። ሴዴቅያስ የግብፅን ርዳታ ለማግኘት በናቡከደናፆር ላይ ዐመፀ ባቢሎናውያንም ፈጣን ርምጃ ወሰዱ፤ ከዚህም የተነሣ በ588 ዓ.ቅ.ክ ላይ ኢየሩሳሌም ተከበበች (ኤር21፥3-7)። በ586 ዓ.ቅ.ክ. ከመደ ምሰሷ በፊት፣ ለሁለት ዓመት ያህል ጥቃቱን ለመከላከል ሞክራለች።

36፥11 *ዐሥራ አንድ ዓመት፤* ከ597-586 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው።

*36፥15-16፤* 24፥19 እና ማብ ይመ።

36፥20-21፤ የሁለቱ ታሪኮች ድምዳሜ መለያየት የሚያስ ደንቅ ነው፤ የመጽሐፈ ሳሙኤልና የመጽሐፈ ነገሥት ጸሓፊ ዎች፣ እስራኤላውያን በምርኮ የተወሰዱት በምን ምክንያት እንደሆነ እንዲሁም በምርኮ እስከተወሰዱበት ጊዜ ድረስ የነበረውን አለመ ታዘዝ፣ በተጨማሪም ራሳቸው ጸሓፊዎቹ የነበሩበት ዘመን ምን እንደሚመስል የማሳየት ፍላጎት ነበራቸው። ይህም እንኳ ጸሓፊው እግዚአብሔር ለዳዊት የገባለትን ቃል ኪዳን (2ነገ 25፥27-30) ለመፈጸም ሲል ለዘሮቹ ያደረገውን በጎነት ገልጾአል የጸሓፊው አስተሳሰብ በመከራ ተፈትነው ያለፉት ቅሬታዎች ወደ ዐላማ ወደ ኋላ መለስ ብሎ በምርኮኞች ላይ ወደ ጸዳችው ምድር መመለሳቸው (ቍ22-23)፣ አዲስ የተስፋ ዘመን መጀመሩን የሚያመለክት ነው። ምርኮውና ስደቱ የመከራን ጊዜት የጨለጠበት ፍርድ ብቻ ሳይሆን፣ ምድሪቱም የሰንበት ዕረፍት ያደረገችበት ዘመን በመሆኑ በረከትም ነው (ዘሌ26፥40-45)። እግዚአብሔር ኪዳኑን አስቦ (ዘሌ26፥45)፣ ሕዝቡን ወደ ቀድሞ ርስታቸው መልሶአቸዋል (የሚቀጥለውን ማብ ይመ)።

*36፥22-23፤* የመጽሐፈ ነገሥቱ ጸሓፊ ታሪኩን የሚደ መድመው፣ ከምርኮ ከመመለስ በፊት ባለው ጊዜ በመሆኑ፣ በዚህ ክፍል የተጻፈውን ታሪክ አልዘገበውም፤ ይሁን እንጂ ይህ ክፍል በመጽሐፈ ዕዝራ መጀመሪያ ላይ (1፥14) ተደግሞ መጻፉ፣ ማለትም ዜና መዋዕሉ ያቆመበትን ሐሳብ መጽሐፈ ዕዝራ ይዞ መነሣቱ፣ የዜና መዋዕሉንና የዕዝራን መጽሐፍ የጻፈው አንድ ሰው ሳይሆን አይቀርም የሚል ግምት አሳድሮአል። የኤር ምያስን ትንቢት ይመ (ኤር25፥1-14) እንዲሁም ከዳን 9 ጋር ያነጻጽሩ። ቂሮስ ከምርኮ ወደ አገራቸው እንዲመለሱ ዐዋጅ ያወጣው ለአይሁድ ሕዝብ ብቻ ሳይሆን ለሌሎችም ምርኮኞች ጭምር ነበር።

# መጽሐፈ ዕዝራ

## መግቢያ

### ዕዝራና ነህምያ

ምንም እንኳ በመጽሐፈ ነህምያ መግቢያ ላይ የሚገኘው "የሐካልያ ልጅ የነህምያ ቃል" (ነህ 1፥1)፣ የሚለው ሐረግ መጽሐፈ ዕዝራና መጽሐፈ ነህምያ፣ በመጀመሪያ ሁለት መጻሕፍት እንደ ነበሩ የሚያመለክት ቢሆንም፣ በጥንት የዕብራይስጥ ቅጆች ላይ ግን አንድ መጽሐፍ ሆነው ቀርበዋል:: ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን (ፍላቪየስ ጆሲፈስ፤ 37-100 ዓ.ም.)እና የአይሁድ ታልሙድ ስለ መጽሐፈ ዕዝራ እንጂ ስለ መጽሐፈ ነህምያ አላወሱም:: ረጅም ዘመን ያላቸው የሰብዓ ሊቃናት (ሰብቱአጀንት) ቅጆች፣ ዕዝራንና ነህምያን የሚያቀርቡት እንደ አንድ መጽሐፍ አድርገው ነው:: ሁለቱን መጻሕፍት 1ኛ ዕዝራና 2ኛ ዕዝራ በማለት ለመጀመሪያ ጊዜ ከሁለት የከፈላቸው አርጌንስ (185-253 ዓ.ም.) ነው:: ጀሮም የላቲኑን ቩልጌት በሚተረጉምበት ጊዜ (390-405 ዓ.ም.)፣ መጽሐፈ ነህምያን ሁለተኛው የኢስድራስ (የዕዝራ) መጽሐፍ ብሎ ሰይሞታል:: በዊክሊፍና (1382) በኮቨርዴል የተዘጋጁት (1535)የእንግሊዝኛ ትርጉሞችም መጽሐፈ ዕዝራን፣ "1ኛ ኤስድራስ"፣ መጽሐፈ ነህምያን ደግሞ "2ኛ ኤስድራስ" በማለት ሰይመዋቸዋል:: እነዚህ መጻሕፍት በዕብራይስጡ ቅጆች ላይ እንደ ሁለት መጻሕፍት ሆነው ለመጀመሪያ ጊዜ የቀረቡት በ1448 ዓ.ም. ነው::

### ሥነ ጽሑፋዊ ቅርጹና ጸሓፊው

እንደ 1ኛ እና 2ኛ ዜና መጻሕፍት ሁሉ፣ የዕዝራና የነህምያ መጻሕፍት የቀረበ ግንኙነት አላቸው:: ሁለቱም መጻሕፍት (1) ስለ ቤተ መቅደሱ ዕቃዎች (ዕዝ1፥9-11)፣ (2)ከምርኮ ስለ ተመለሱት ሰዎች (በዚህ ርእስ ላይ ዕዝ 2፤ ነህ 7፥6-73 ጋር ተመሳሳይ ነው)፣ (3) ስለ ዕዝራ የትውልድ ሐረግ (ዕዝ 7፥1-5)፣ (4) ስለ ነገድ አለቆች (ዕዝ 8፥1-14)፣ (5)ከአሕዛብ ጋር ስለ ተጋቡት ሰዎች (ዕዝ10፥18-43)፣ (6)ቅጥሩን በመሥራት ስለ ተባበሩትና ስለ ረዱት ሰዎች (ነህ3)፣ (7)ኪዳኑን ስላተሙት (ነህ10፥1-27)፤ (8)በኢየሩሳሌምና በሌሎች ከተሞች ስለሚኖሩት ሰዎች (ነህ11፥3-36)እንዲሁም (9)ስለ ካህናትና ስለ ሌዋውያን (ነህ 12፥1-26) ያወሳሉ::

ከዚህ በተጨማሪ በመጽሐፈ ዕዝራ ውስጥ ሰባት ዐበይት ሰነዶች ወይም ደብዳቤዎች ይገኛሉ (ከመጀመሪያው በስተቀር የቀሩት በሙሉ የተጻፉት በአረማይስጥ ቋንቋ ነው፤ የመጀመሪያው የተጻፈው በዕብራይስጥ ቋንቋ ነው):: ሰነዶቹም የሚከተሉት ናቸው፤ (1)የቂሮስ ዐዋጅ (1፥2-4)፤ (2)ሬሁምና ተባባሪዎቹ በአይሁድ ላይ ያቀረቡት ክስ (4፥11-16)፤ (3) የቀዳማዊ አርጤክስስ መልስ (4፥17-22)፤ (4) ከተንትናይ የመጣው ዘገባ (5፥7-17)፤ (5)ቂሮስ የሰጠው ትእዛዝ (6፥2-5)፤ (6)ዳርዮስ ለተንትናይ የጻፈው መልስ (6፥6-12)እና (7)ቀዳማዊ አርጤክስስ ለዕዝራ የሰጠው ሥልጣን (7፥12-26):: እነዚህ መዛግብት በፋርስ ዘመነ መንግሥት ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ከተጻፉት ከሌሎች ሰነዶችና ደብዳቤዎች ጋር ተመሳሳይ ቅርጽና ይዘት እንዳላቸው ተረጋግጧል::

በመጽሐፈ ዕዝራ ውስጥ የሚገኙ አንዳንድ ክፍሎች የራሱ የዕዝራ ታሪክ በመሆናቸው በአንደኛ መደብ ነጠላ ቍጥር ተጽፈዋል (7፥27–28፤8፥1–34፤9):: ሌሎቹ ክፍሎች የተጻፉት ደግሞ በሦስተኛ መደብ ነው (7፥1–26፤10 እንዲሁም ነህ 8 ይመ):: ሥነ ልሳናዊ ትንታኔዎች እንዳረጋገጡት፣ በአንደኛና በሦስተኛ መደብ የተጻፉት ክፍሎች ተመሳሳይ ይዘት ያላቸው በመሆኑ ሁለቱም ክፍሎች የተጻፉት በአንድ ሰው እንደ ሆነ ያመለክታል::

በርካታ ሊቃውንት፣ መጽሐፈ ዕዝራና መጽሐፈ ነህምያ የተጻፉት 1ኛ እና 2ኛ ዜና መዋዕልን በጻፈው ሰው እንደ ሆነ ይናገራሉ:: ይህ አመለካከት የተመሠረተው መጽሐፈ ዜና መዋዕልም ሆነ ዕዝራ - ነህምያ የሚጋሩት ተመሳሳይ ነገር አላቸው በሚለው እሳቤ ላይ ነው:: ይኸውም በመጽሐፈ ዜና መዋዕል መጨረሻና በመጽሐፈ ዕዝራ መጀመሪያ ላይ የሚገኙት ቍጥሮች የያዙት ተመሳሳይ ሐሳብ ነው:: መጽሐፈ ዜና መዋዕልም ሆነ ዕዝራ-ነህምያ ስለ ስም ዝርዝሮች፣ ስለ ሃይማኖታዊ በዓሎች፣ ስለ "ቤተ ሰብ መሪዎች"፣ ስለ "እግዚአብሔር ቤት" ትኵረት በመስጠት ጽፈዋል:: በመጻሕፍቱ ውስጥ በተለይ ልዩ ትኵረት የተሰጠው ስለ ሌዋውያንና ስለ ቤተ መቅደሱ አገልጋዮች ነው:: "ዘማሪዎች"፣ "በር ጠባቂዎች" እና "የቤተ መቅደስ አገልጋዮች" የሚሉት ቃላት ብዙ ጊዜ የተጠቀሱት በዕዝራ-ነህምያና በዜና መዋዕል መጻሕፍት ውስጥ ነው:: የ1ኛ ዜና መዋዕልን መግቢያ ይመ::

### መጽሐፉ የተጻፈበት ጊዜ

መጽሐፈ ዕዝራ በ440 ዓ.ቅ.ክ ገደማ፣ ነህምያ ደግሞ በ430 ዓ.ቅ.ክ ላይ እንደ ተጻፉ ይገመታል::

### የመጽሐፈ ዕዝራና የመጽሐፈ ነህምያ ቅደም ተከተል

በትውፊታዊው አመለካከት መሠረት ዕዝራ ወደ ኢየሩሳሌም የመጣው (ዕዝ 7፥8)፣ ቀዳማዊ አርጤክስስ በነገሠ በሰባተኛው ዓመት (458 ዓ.ቅ.ክ.) ሲሆን፣ ነህምያ ደግሞ በ20ኛው ዓመት (445 ዓ.ቅ.ክ. ነህ 2፥1) ነው::

አንዳንዶች ይህን ቅደም ተከተል ገልብጠው ነህምያ ወደ ኢየሩሳሌም የመጣው በ445 ዓ.ቅ.ክ. ሲሆን፣ ዕዝራ ደግሞ ዳግማዊ አርጤክስስ በነገሠ በሰባተኛው ዓመት (398 ዓ.ቅ.ክ.) ነው ይላሉ:: "በሰባተኛው" (ዕዝራ7፥8) የሚለውን "በሃያ ሰባተኛው" ወይም "በሠላሳ ሰባተኛው" በሚለው በማስተካከል ዕዝራን

ከነህምያ በማስከተል ነው። ሆኖም ሁለቱም በአንድ ዘመን የነበሩ ሰዎች እንደ ሆኑ ይናገራሉ።

እነዚህ አማራጭ አመለካከቶች ከትውፊታዊው አመለካከት ይልቅ ብዙ ችግር አለባቸው። መጽሐፉ እንደሚናገረው ዕዝራ ወደ ኢየሩሳሌም የመጣው ከነህምያ በፊት ነው። በነህ 8፥9 ላይ (የሙሴ ሕግ ሲነበብ፣) እንዲሁም በነህ 12፥26:36 ላይ (የኢየሩሳሌም ቅጥር ሲመረቅ) ሁለቱም አብረው ተገኝተዋል። በገጽ 675 ላይ ያለውን የዕዝራ-ነህምያ ቅደም ተከተል የሚለውን ይመ።

### መጽሐፉ የተጻፈበት ቋንቋ

ከዕዝራ 4፥8-6፥18፤7፥12-26 በስተቀር መጽሐፈ ዕዝራና መጽሐፈ ነህምያ የተጻፉት በዕብራይስጥ ቋንቋ ነው። እነዚህ ክፍሎች የተጻፉት በፋርስ ዘመነ መንግሥት ዓለም አቀፍ ቋንቋ በነበረው በአረማይስጥ ነው።




### አስተዋፅኦ

1. ከምርኮ በመጀመሪያ የተመለሱትና የቤተ መቅደሱ መታደስ (ም1-6)
   - ሀ. ከምርኮ በመጀመሪያ የተመለሱት ሰዎች (ም1)
     1. የቂሮስ ዐዋጅ (1፥1-4)
     2. ከሰሳብሳር ጋር የተመለሱት ሰዎች (1፥5-11)
   - ለ. ከምርኮ የተመለሱ ሰዎች ስም ዝርዝር (ም2)
   - ሐ. የቤተ መቅደሱ አምልኮ ማንሰራራት (ም3)
     1. የመሠዊያው እንደ ገና መሠራት (3፥1-3)
     2. የዳስ በዓል (3፥4-6)
     3. የቤተ መቅደሱ ሥራ እንደ ገና መጀመር (3፥7-13)
   - መ. ሕንፃው እንዳይሠራ የተደረገ ተቃውሞ (4፥1-23)
     1. በቂሮስ ዘመነ መንግሥት የተነሣው ተቃውሞ (4፥1-5)
     2. በአርጤክስስ ዘመነ መንግሥት የተነሣው ተቃውሞ (4፥6)
     3. በቀዳማዊ አርጤክስስ ዘመነ መንግሥት የተነሣው ተቃውሞ (4፥7-23)
   - ሠ. የቤተ መቅደሱ ሥራ መፈጸም (4፥24-6፥22)
     1. በዳርዮስ ዘመነ መንግሥት ሥራው እንደ ገና መጀመሩ (4፥24)
     2. በሐጌና በዘካርያስ አነሣሽነት የታየው አዲስ ጅማሬ (5፥1-2)

## ቂሮስ ምርኮኞቹ እንዲመለሱ ፈቀደ

1፥1-3 ተጓ ምብ 2ዜና 36፥22-23

**1** ቂሮስ የፋርስ ንጉሥ በሆነ በመጀመሪያው ዓመት እግዚአብሔር የቂሮስን መንፈስ አነሣሥቶ በመንግሥቱ ሁሉ ዐዋጅ እንዲያስነግርና ይህም በጽሑፍ እንዲሰፍር አደረገ፤ ይህ የሆነው በኤርምያስ አፍ የተነገረው የእግዚአብሔር ቃል ይፈጸም ዘንድ ነው::

[2]የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ የሚለው ይህ ነው፤

" 'የሰማይ አምላክ እግዚአብሔር የምድርን መንግሥታት ሁሉ ሰጥቶኛል፤ በይሁዳ ምድር በምትገኘው በኢየሩሳሌምም ለእርሱ ቤተ መቅደስ እንድሠራ አዞኛል:: [3]ከሕዝቡ መካከል በእናንተ ዘንድ የሚኖር ማናቸውም ሰው አምላኩ ከእርሱ ጋር ይሁን፤ በይሁዳ ወደምትገኘው ወደ ኢየሩሳሌም ይውጣና በዚያ ለሚኖረው አምላክ፣ ለእስራኤል አምላክ ለእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ይሥራ፤ [4]ባለበት ስፍራ የሚቀሩ በየትኛውም አገር የሚኖሩ ሰዎች ሁሉ በኢየሩሳሌም ለሚገኘው የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ስጦታ እንዲሆን በበጎ ፈቃድ ከሚያቀርቡት መባ በተጨማሪ ብርና ወርቅ፣ ዕቃና እንስሳ በመስጠት ይርዷቸው' "

[5]ከዚያም አምላክ መንፈሳቸውን ያነሣሣው የይሁዳና የብንያም ቤተ ሰብ አለቆች እንዲሁም ካህናቱና ሌዋውያኑ ሁሉ ለመሄድና በኢየሩሳሌም የሚገኘውን የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ለመሥራት ተዘጋጁ:: [6]ጎረቤቶቻቸውም ሁሉ በበጎ ፈቃድ ከሰጡት መባ በተጨማሪ ከብርና ከወርቅ የተሠሩ ዕቃዎችን፣ ቊሳቍስን፣ እንስሶችንና ሌሎች ጠቃሚ የሆኑ ስጦታዎችንም በመለገስ ረዷቸው:: [7]ከዚህም በላይ ንጉሡ ቂሮስ፣ ናቡከደነፆር ከኢየሩሳሌም ወስዶ በአማልክቱ ቤተ ጣዖት[ሀ] ያኖራቸውን የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ንዋያተ ቅድሳት አወጣ:: [8]የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ በግምጃ ቤቱ ኀላፊ በሚትሪዳጡ አማካይነት ንዋያተ ቅድሳቱ እንዲመጡና በይሁዳው ገዥ በሰሳብሳር ፊት እንዲቈጠሩ አደረገ።

[9]የዕቃው ዝርዝር ይህ ነበር፤

| | |
|---|---|
| የወርቅ ሳሕን | 30 |
| የብር ሳሕን | 1,000 |
| ዝርግ የብር ሳሕን[ለ] | 29 |

1፥1 ዕዝ6፥22፤7፥27፤ ኤር25፥11-12፤ 29፥10-14፤ዘካ1፥12-16
1፥2 መሳ4፥10፤ መዝ72፥11ኢሳ41፥2፡ 25፤44፥28፤45፥13፤ 46፥11፤49፥ 7-23፤ 60፥3፡10፤ ሐጌ1፥2
1፥4 ዘፀ3፥22፤ ዘኍ15፥3፤ዕ3፥7፤ 4፥3፤5፥13፤6፥3፡14፤ መዝ50፥14፤54፥6፤ 116፥17፤72፥8-11፤ ኢሳ10፥20-22፤ ራእ21፥24
1፥5 ቍ1፤ ዘፀ35፥20-22፤2ዜና11፥1፡ 3፡10፡12፡23፤15፥2፡8 9፤ 25፥5፤31፥1፤34፥9፤ 36፥22፤ዕዝ4፥1፤10፥9፤ ነህ11፥4፤12፥34፤ መዝ127፥1፤ሐጌ1፥14፤ ፊል2፥13
1፥6 ዘፀ3፥22
1፥7 2ነገ24፥13፤ 2ዜና36፥7፡10፤ዕዝ5፥14፤ 6፥5፤ ኤር52፥17-19
1፥8 1ዜና3፥18

[ሀ]7 ወይም፣ አምላኩ
[ለ]9 በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጒም በትክክል አይታወቅም::

*1፥1-3፤* ይህ ክፍል ከ2ዜና መጽሐፍ የመጨረሻዎቹ ሁለት ቍጥሮች ጋር አንድ ዐይነት ነው:: ከዚህም የተነሣ መጻሕፍት ዜና መዋዕል፣ ዕዝራና ነህምያ የተጻፉት እና/ወይም የታረሙት፣ በአንድ ሰው ይኸውም ጸሓፊ ዜና መዋዕል እየተባለ በሚጠራው ሰው እንደሆነ በሰፊው ይነገራል። ይሁን እንጂ እዚህ ላይ ተደግሞ መገኘቱ የመጽሐፊ ዜና መዋዕል ጸሓፊ ድርጊቶቹን ባፈጸጸማቸው የጊዜ ቅደም ተከተል መሠረት ለማያያዝ ያደረገው ዘዴ ሳይሆን አይቀርም::

1፥1 ***በመጀመሪያው ዓመት፤*** ንጉሥ ቂሮስ ባቢሎንን በጥቅምት ወር 539 ዓ.ቅ.ክ ላይ ማርኮ ከያዘ በኋላ፣ ከመጋቢት ወር 538 ዓ.ቅ.ክ አንሥቶ ባቢሎንን መግዛት እስከ ጀመረበት ጊዜ ነው:: የፋርስ ግዛተ አፄ መሥራች የሆነው ቂሮስ በፋርስ ላይ የነገሠው ከ559-530 ዓ.ቅ.ክ ነበር:: በኢሳ 44፥28፤ 45፥1 ላይ እግዚአብሔር ቂሮስን "እረኛ" እንዲሁም "የቀባሁት" ይለዋል:: ***በኤርምያስ አፍ የተነገረው የእግዚአብሔር ቃል ይፈጸም ዘንድ፤*** ኤርምያስ የሰባ ዓመቱን ምርኮ ተንብዮ ነበር (ኤር 25፥11-12፤ 29፥10):: ሕዝቡ በመጀመሪያ ተማርኮ የሄደው በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት በሦስተኛው ዓመት በ605 ዓ.ቅ.ክ ነበር (ዳን 1፥1):: በ538 ዓ.ቅ.ክ ማለትም በግምት ከሰባ ዓመት በኋላ ወደ ገዛ አገሩ መመለስ ጀመረ::

*1፥2-4፤* ይህ በቃል የተነገረው የቂሮስ ዐዋጅ የተጻፈው በምርኮኞቹ በእስራኤላውያን ቋንቋ ማለትም በዕብራይስጥ ነበር፤ በ6፥3-5 ላይ የሚገኘውና ግልባጩም በቤተ መዛግብት እንዲቀመጥ የተደረገው ዋናው የዐዋጅ ቃል የተጻፈው ግን በኦረማይስጥ ቋንቋ ነበር።

1፥2 ***የሰማይ አምላክ፤*** ይህ ሐረግ በብሉይ ኪዳን የተጠቀሰው ሀያ ሁለት ጊዜ ሲሆን፣ ከዚህ ውስጥ ዐሥራ ሰባቱ የተጠቀሰው በዕዝራ፣ በነህምያና በትንቢተ ዳንኤል መጻሕፍት ውስጥ ነው:: ***በኢየሩሳሌም ለእርሱ ቤተ መቅደስ፤*** ኢየሩሳሌምና የእግዚአብሔር ቤት በዕዝራና በነህምያ መጻሕፍት ውስጥ ጎልተው የሚታዩ አርእስተ ጒዳዮች ናቸው::

*1፥3፤* ቂሮስ ከእርሱ በፊት እንደ ነበሩት አሦራውያንና ባቢሎናውያን ድል ያደረጓቸውን ሕዝቦች አማልክት ምስል በመውሰድ ፈንታ የሚገዟቸውን ሕዝቦች አማልክት የማያስቈጣ መመሪያ አውጥቶ ነበር:: ለአይሁድም ሕዝብ ያሳየው ልግስና ለባቢሎናውያን ከነበረው ቅን አመለካከት ጋር የሚነጻጸር ነበር::

1፥4 ***በየትኛውም አገር የሚኖሩ ሰዎች ሁሉ፤*** ምናልባት ከመስጴጦምያ ለመውጣት ያልፈለጉ አይሁዳውያን ሳይሆኑ አይቀርም:: ***በበጎ ፈቃድ ... በመስጠት፤*** የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስና ሥርዐቱ እንደ ገና ሊታደስ የሚችለው በዚህ ዐይነት መሆኑን የሚያመለክት አባባል ነው (2፥68፤ 3፥5፤8፥28 ይመ)::

1፥5 ***የይሁዳና የብንያም፤*** ባቢሎናውያን ከማረኳቸው ከይሁዳ መንግሥት ነገዶች ዋናዎቹ እነዚህ ሁለቱ ነበሩ:: ***የቤተ ሰብ አለቆች፤*** በጥንት ዘመን ቤተ ሰብ ሲባል፣ ከአንድ የዘር ግንድ የወረዱትን ብዙ ቤተሰቦች ያጠቃልል ነበር፤ በአጭሩ ጐሣ እንደ ማለት ነው:: የቤተ ሰቡ መሪ "የቤተ ሰብ አለቃ" ነው (10፥16 ይመ፤ በተጨማሪም 2፥59፤ ነህ 7፥61፤ 10፥34 ይመ)::

*1፥7፤* በጥንት ዘመን ድል ያደረጉ ነገሥታት ድል ያደረጓቸውን ከተሞች አማልክት ምስሎች ማርኮ መውሰድ የተለመደ ነበር:: አይሁድ ግን የእግዚአብሔር ምስል የሚባል ነገር ስላልነበራቸው (የዘፀ. 20፥4 ማብ ይመ)፣ ናቡከደነፆር ይዞ የሄደው የቤተ መቅደሱን ዕቃዎች ብቻ ነበር::

1፥8 ***ሚትሪዳጡ፤*** የፋርሶች ስም ሲሆን፣ ትርጒሙም "ለሚትራ የተሰጠ" ማለት ነው፤ "ሚትራ" በሁለተኛው ምእተ ዓ.ቅ.ክ. በሮማውያን ወታደሮች ዘንድ እጅግ የታወቀ የፋርስ ሰዎች ጣዖት ነበር:: ***ሰሳብሳር፤*** የባቢሎኖች ስም ሲሆን፣ ትርጒሙም "ሲን አባትን ይጠብቅ" ወይም "ሸማሽ ሻሹ አባትን ይጠብቅ" ማለት ነው፤ "ሲን" የጨረቃ አምላክ ሲሆን "ሸማሽ" ወይም "ሻሹ" ደግሞ የፀሓይ አምላክ ነው:: ሰሳብሳር ስሙ የባቢሎናውያን ቢሆንም በሰማርያ አስተዳዳሪ ሥር በነበረችው የይሁዳ ምክትል ገዥ የነበረ አይሁዳዊ ባለሥልጣን ሳይሆን አይቀርም (5፥14 ይመ):: አንዳንድ ሰዎች ሰሳብሳርን ዘሩባቤል ነው ይላሉ፤ ለዚህም የሚያቀርቡት ምክንያት የሚከተለው ነው፤ (1) ሁለቱም ሰዎች ገዦች ነበሩ (5፥14፤ ሐጌ 1፥1፤ 2፥2)፤ (2) ሁለቱም የቤተ መቅደሱን መሠረት የጣሉ ሰዎች ነበሩ (3፥2-8፤ 5፥16፤ ሐጌ 1፥14-15፤ ዘካ 4፥6-10)፤ (3) በባቢሎን የነበሩ አይሁድ የባቢሎናውያን "የሹመት" ስም ይሰጣቸው ነበር (ከዳን 1፥7 ጋር ያነጻጽሩ)፤ (4) የሴፍ ወልደ ኮርዮን (ጆሲፈስ) የተባለው ታሪክ ጸሓፊ፣ በመጽሐፉ ውስጥ ሰሳብሳርንና ዘሩባቤልን አንድ ሰው አድርጎ ያቀረባቸው ይመስላል ("አንቲኪውቲስ" 11.1.3):: ሌሎች ደግሞ የአዋልድ መጻሕፍት ሁለት የተለያዩ ሰዎች አድርገው ስለሚያቀርቧቸው (1ዕዝራ ካልዕ 6፥18)፣ ሁለት የተለያዩ ሰዎች ናቸው ይላሉ:: ከዚህም በላይ ከምርኮ በሚመለሱበት ጊዜ፣ የሰሳብሳር ዕድሜ ትልቅ የዘሩባቤል ደግሞ ትንሽ ሳይሆን አይቀርም። እንዲሁም ሰሳብሳር የመንግሥት ባለሥልጣን፣ ዘሩባቤል ግን አንድ የታወቀ መሪ ብቻ ሊሆን ይችላል (3፥8-11):: በሌላ በኩል ደግሞ የዘሩባቤል ስም ከሊቀ ካህናቱ ከኢያሱ ስም ጋር አብሮ ሲጠቀስ፣ ከሰሳብሳር ጋር ግን አንድም ካህን አልተጠቀሰም:: የቤተ መቅደሱ መሠረት በ536 ዓ.ቅ.ክ. ሲጣል፣ ሰሳብሳር የሥራው መሪ ቢሆንም፣ የተሠራው ሥራ እጅግ አነስተኛ በመሆኑ፣ ከዐሥራ ስድስት ዓመት በኋላ የቤተ መቅደሱ መሠረት ለሁለተኛ ጊዜ ሲሠራ ዘሩባቤል ሥራውን መምራት ነበረበት (ሐጌ 1፥14-15፤ዘካ 4፥6-10 ይመ):: ከዚህም በቀር ሰሳብሳርና ሺናጻር (1ዜና 3፥18) የአንድ ሰው ስም መሆኑን የሚናገሩ አሉ፤ ይህ ሼናጻር የተባለው ሰው የንጉሡ የኢኮንያን አራተኛ ወንድ ልጅ ነበር:: ይህ እንዲህ ከሆነ፣ ዘሩባቤል የሰሳብሳር የወንድም ልጅ ነበር ማለት ነው (3፥2 ከ1ዜና 3፥18 ጋር ያነጻጽሩ)::

*1፥9-11፤* አሦራውያንና ባቢሎናውያን ድል ሲያደርጉ፣ ድል ያደረጓቸውን ሕዝቦች ንብረት ዘርፈው ሲሄዱ ጸሐፊዎቻቸው ደግሞ በምርኮ የተበዘበዘውን የዕቃ ዝርዝር በጥንቃቄ ይመዘግቡ ነበር:: በቍ 9-10 ላይ የተዘረዘረው የዕቃ ብዛት 2499 እንጂ፣ በቍ 11 ላይ

## የሁነቶች/የጊዜ ቅደም ተከተል ዕዝራ-ነህምያ

ከዚህ በታች የቀረቡ ቀናት እንደ ዕብራውያኑ አቈጣጠር ነው ፡

540 530 520 510 500 490 480 470 460 450 440

| ዓመት | ወር | ቀን 2 | ክስተት | የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል |
|---|---|---|---|---|
| 539 | ጥቅምት | 15 2 | የባቢሎን መማረክ | ዳን 5፥30 |
| 538 537 | ከመጋቢት እስከ መጋቢት | | የቂሮስ የመጀመሪያ ዓመት | ዕዝ 1፥1-4 |
| 537(?) | | | ከምርኮ መመለስ | ዕዝ 1፥11 |
| 537 | 7ኛ | | የመሠዊያው መሠራት | ዕዝ 3፥1 |
| 536 | 2ኛ | | የቤተ መቅደሱ ሥራ ተጀመረ | ዕዝ 3፥8 |
| 536ጠ530 | | | በቂሮስ ዘመን የተነሣ ተቃውሞ | ዕዝ 4፥1-5 |
| 530ጠ520 | | 24 | የቤተ መቅደሱ ሥራ መቆም | ዕዝ 4፥24 |
| 520 | 6ኛ = መስከረም | 11 3 | በዳርዮስ ዘመን የቤተ መቅደሱ ሥራ ተጀመረ | ዕዝ 5፥2፤ ሐጌ 1፥14 |
| 516 | 12ኛ = መጋቢት | 3 1 30 | የቤተ መቅደሱ ሥራ ተጠናቀቀ | ዕዝ 6፥17 |
| 458 | 1ኛ = መጋቢት | 1 28 | የዕዝራ ከባቢሎን መውጣት | ዕዝ 7፥6-9 |
| | 5ኛ = ሐምሌ | 20 19 | የዕዝራ ኢየሩሳሌም መድረስ | ዕዝ 7፥8-9 |
| | 9ኛ = ታህሳስ | 1 19 | የህዝብ ጉባዔ | ዕዝ 10፥9 |
| | 10ኛ = ታህሳስ | 18 | የምርመራው ጅማሬ | ዕዝ 10፥16 |
| 457 | 1ኛ = መጋቢት | 5 24 | የምርመራው ፍጻሜ | ዕዝ 10፥17 |
| 445 444 | ከሚያዝያ እስከ መጋቢት | | የቀዳማዊ አርጤክስስ 20ኛ ዓመት | ነህ 1፥1 |
| 445 | 1ኛ = ከመጋቢት-ሚያዝያ | | የነህምያ ወደ ንጉሡ መግባት | ነህ 2፥1 |
| | = ነሐሴ (?) | 25 11 | የነህምያ ወደ ኢየሩሳሌም መድረስ | ነህ 2፥11 |
| | 6ኛ = መስከረም | 27 25 | የቅጥሩ ሥራ መጠናቀቅ | ነህ 6፥15 |
| | 7ኛ=መስከረም እስከ ጥቅምት | 15 ጠ 22 12 ጠ 18 | የሕዝብ ጉባዔ | ነህ 7፥73-8፥1 |
| | 7ኛ = ጥቅምት | 24 20 | የዳስ በዓል | ነህ 8፥14 |
| | 7ኛ = ጥቅምት | 23 3 | ጾም | ነህ 9፥1 |
| 433 432 | መጋቢት እስከ ሚያዝያ | | የአርጤክስስ 32ኛ ዓመት፤ የነህምያ በንጉሡ መጠራትና መመለስ | ነህ 5፥14፤13፥6 |

[10]ጐድጓዳ የወርቅ ሳሕን 30
ባለ ግጣም የብር
ጐድጓዳ ሳሕን 410
ሌሎች ቁሳቍስ 1000

[11]ባጠቃላይ አምስት ሺህ አራት መቶ የወርቅና የብር ዕቃዎች ነበሩ። ሰሳብሳር ምርኮኞቹ ከባቢሎን ወደ ኢየሩሳሌም ሲመለሱ ይህን ሁሉ ዕቃ ይዞ ወጣ።

## ወደ አገራቸው የተመለሱ ምርኮኞች ዝርዝር

2፥1-70 ተጓ ምብ ነህ 7፥6-73

2 የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ወደ ባቢሎን ማርኮ ከወሰዳቸው መካከል ከምርኮ ተመል ሰው ወደየራሳቸው ከተሞች፣ ወደ ይሁዳና ወደ ኢየሩሳሌም የመጡት የአገሩ ልጆች እነዚህ ናቸው፤ [2]የመጡትም ከዘሩባቤል፣ ከኢያሱ፣ ከነህምያ፣ ከሠራያ፣ ከረዕላያ፣ ከመርዶክዮስ፣ ከበላሳን፣ ከመሲፋር፣ ከበጉዋይ፣ ከሬሁም፣ ከበዓና ጋር ነበር።

የተመለሱት የእስራኤል ሰዎች ዝርዝር የሚከተለው ነው፤

[3]የፋሮስ ዘሮች 2,172
[4]የሰፋጥያስ ዘሮች 372
[5]የኤራ ዘሮች 775
[6]ከኢያሱና ከኢዮአብ ዘር
የሆኑት የፈሐት ሞዓብ ዘሮች 2,812
[7]የኤላም ዘሮች 1,254
[8]የዛቱዕ ዘሮች 945
[9]የዘካይ ዘሮች 760
[10]የባኒ ዘሮች 642
[11]የቤባይ ዘሮች 623
[12]የዓዝጋድ ዘሮች 1,222
[13]የአዶኒቃም ዘሮች 666
[14]የበጉዋይ ዘሮች 2,056
[15]የዓዲን ዘሮች 454
[16]የሕዝቅያስ ልጅ የአጤር ዘሮች 98
[17]የቤሳይ ዘሮች 323
[18]የዮራ ዘሮች 112
[19]የሐሱም ዘሮች 223
[20]የጋቤር ዘሮች 95
[21]የቤተ ልሔም ሰዎች[ሐ] 123
[22]የነጦፋ ሰዎች 56
[23]የዓናቶት ሰዎች 128
[24]የዓዝሞት ዘሮች 42
[25]የቂርያትይዓሪም[መ]፣
የከፊራና የብኤሮት ዘሮች 743
[26]የራማና የጌባ ዘሮች 621
[27]የማክማስ ሰዎች 122
[28]የቤቴልና የጋይ ሰዎች 223
[29]የናባው ዘሮች 52
[30]የመጌብስ ዘሮች 156
[31]የሌላው ኤላም ዘሮች 1,254
[32]የካሪም ዘሮች 320
[33]የሎድ፣ የሐዲድና
የኦኖም ዘሮች 725
[34]የኢያሪኮ ሰዎች 345
[35]የሴናዓ ዘሮች 3,630
[36]ካህናቱ፦
ከኢያሱ ቤተ ሰብ
የዮዳኤ ዘሮች 973

2፥1 ቍ 70፤ 2ነገ24፥16፤25፥12፤ 1ዜና9፥2፤2ዜና36፥20፤ ነህ7፥73፤11፥3
2፥2 1ዜና3፥19፤ 6፥14፤ዕዝ3፥2፤5፥2፤ 10፥18፤ነህ10፥2፤ 11፥11፤12፥1፡8፤ ሐጌ1፥1፡12፤2፥4፤ ዘካ3፥1-10፤ 6፥9-15፤ ማቴ1፥12፤ሉቃ3፥27
2፥3 ዕዝ8፥3፤ 10፥25፤ ነህ3፥25
2፥13 ዕዝ8፥13
2፥21 ሚክ5፥2
2፥26 ኢሱ18፥25
2፥28 ዘፍ12፥8
2፥34 1ነገ16፥34፤ 2ዜና28፥15
2፥36 1ዜና24፥7

[ሐ]21 ወይም *ልጆች፣ ዘሮች*
[መ]25 የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም (እንዲሁም ነህ 7፥29 ይመ)፤ ዕብራይስጡ ግን፣ ቂሪያት አሪም ይላል።

እንደ ተገለጸው 5400 አይደለም። ይህ የሆነው ምናልባት ትልቅና ውድ የሆኑትን ዕቃዎች ብቻ ስለመዘገቡ ሊሆን ይችላል።

*1፥11፤* ሰሳብሳር በ537 ዓ.ቅ.ክ ስላደረገው ጕዞ የሚገልጽ ዝርዝር መግለጫ አልተሰጠንም። በኋላ ግን ዕዝራ ካደረገው ጕዞ (7፥8-9) ለመረዳት እንደሚቻለው፣ መንገዱ አራት ወር ያህል ይፈጅ ነበር። በዚህ መጽሐፍ መጨረሻ ላይ የሚገኘውን ካርታ ቁ 7 ይመ።

*2፥1-70፤* በም 2 ላይ የተጠቀሰው ዝርዝር አብዛኛው በነህ 7፥6-73 ላይ ካለው ዝርዝር ጋር በጣም ተመሳሳይ ነው (በተጨማሪም በአዋልድ መጽሐፍ ላይ 1ኛ ኢድራስ 5፥4-46 ይመ)፡ የየመንደሩ ስም ዝርዝር እንደሚያመለክተው፣ ሰዎቹ የተወለዱባቸውን ቦታዎች አልረሱም። ከዚህም በላይ ከምርኮ የተመለሱት ከየነገዱ፣ ከየቀበሌውና ከየከተማው እንደ ነበሩ ያመለክታል። በዚህ ክፍል ያለው ዝርዝር ከነህ 7 ጋር ሲነጻጸር ብዙ የስምና የቍጥር ልዩነት እንዳለው ያሳያል። ለምሳሌ በዕዝራና በነህምያ መጻሕፍት መካከል እንዷ ሀያ በመቶ ያህል የቍጥር ልዩነት አለ። እነዚህ ልዩነቶች ሊፈጠሩ የቻሉት ቍጥሮች በምስጢራዊ ትእምርቶች ከመጻፋቸው የተነሣ ነው፤ ይኸውም በመጀመሪያው ቅጆች ላይ አምዳዊ ነቍጣዎችን ለአንድ፣ አግድማዊ ነቍጣዎችን ለዐሥር መጠቀማቸው ቅጆችን የሚገለብጡ ሰዎች ስሕተት እንዲፈጽሙ ሳያደርጋቸው አልቀረም።

2፥1 *የክፍለ አገሩ፤* ምናልባት ይሁዳን ነው (ከ5፥8 ጋር ያነጻጽሩ፤ በተጨማሪም ነህ 1፥3 ይመ)።

2፥2 *ከዘሩባቤል፤* የ3፥2፤ 5፥2 ማብ ይመ። *ከኢያሱ፤* የስሙ ትርጕም፣ "እግዚአብሔር ያድናል" ማለት ነው። በግሪኩ "ኢየሱስ" ማለት ነው (የማቴ 1፥21 አማራጭ ትርጕሙን ይመ)። *ከነህምያ፤* ይህ ነህምያ በነህምያ መጽሐፍ ውስጥ የተጠቀሰው ሰው አይደለም። *ከመርዶክዮስ፤* "ማርዱክ" ከተባለው የባቢሎን ጣዖት የተገኘ ስም ነው (ከኤር 50፥2 ጋር ያነጻጽሩ)፡ የንግሥት አስቴር አጎትም በዚህ ስም ይጠራ ነበር (አስ 2፥7)፡

2፥3 *የፋሮስ፤* "ቍንጫ" ማለት ነው (በእስራኤላውያን ዘንድ በተባዮችና በእንስሳት ስም መጠራት የተለመደ ነበር)፡ የዚህ ቤተ ሰብ አባላትና ሌሎችም በቍ 6-14 የተጠቃሱት ቤተ ሰቦች ከዕዝራ ጋር ተመልሰዋል (8፥3-14)።

2፥5 *የኤራ፤* ምናልባት፣ "የዱር በሬ" ማለት ይሆናል፤ በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ እንዲህ ያለው ስም እምብዛም አይታወቅም፤ ነገር ግን በመስጴጦምያ ሰነዶች ላይ ስሙ በመገኘቱ በምርኮ ዘመን የተወረሰ ሳይሆን አይቀርም።

2፥6 *ፈሐት ሞዓብ፤* ትርጕሙ፣ "የሞዓብ ገዥ" ማለት ሲሆን፣ ይህ ስም ምናልባት በአንድ ወቅት የማዕረግ ስም ሆኖ ሳያገለግል አልቀረም።

2፥12 *ዓዝጋድ፤* ከ8፥12 ጋር ያነጻጽሩ፤ የቃሉ ትርጕም፣ "ጋድ ብርቱ ነው" ማለት ሲሆን፣ ይህ ስም ምናልባት 'ጋድ' ከተባለው ከዕድል ወይም ከጋድ አምላክ ጋር (ኢሳ 65፥11) ወይም ከዮርዳኖስ ማዶ ከሰፈረው ከጋድ ነገድ ጋር የተያያዘ ሊሆን ይችላል።

2፥16 *የአጤር፤* በመሳ 3፥15፤ 20፥16 ላይ እንደተገለጸው የስሙ ትርጕም፣ "ግራኝ" ማለት ነው።

*2፥21-35፤* ከቍ 3-20 ያለው የቤተ ሰብ ስም ዝርዝር ሲሆን፣ ከቍ 21–35 ያለው ግን ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን በብንያም ምድር የሚገኙት የመንደርና የከተማ ስሞች ዝርዝር ነው። ከይሁዳ በስተ ደቡብ በነጌብ የነበሩ ከተሞች አለመጠቀሳቸው አስገራሚ ነገር ነው። ናቡከደነፆር ይሁዳን በ597 ዓ.ቅ.ክ በወረረ ጊዜ (ኤር 13፥19)፣ የኤዶምያስ ሰዎች ሁኔታውን በመጠቀም ያንን ስፍራ ሊይዙ ችለዋል (ትንቢተ አብድዩ ይመ)።

2፥21 *የቤተልሔም ሰዎች፤* ጌታ ኢየሱስ የተወለደው ከእነዚሁ ከምርኮ ከተመለሱት የቤተልሔም ሰዎች ዘር ሊሆን ይችላል።

2፥23 *የዓናቶት፤* የኤር 1፥1 ማብ ይመ።

2፥28 *የቤቴልና፤* የዘፍ 12፥8 ማብ ይመ። እንደ ቤቴል፣ ምጽጳ፣ ገባዖንና ጊብዓን የመሳሰሉት ከተሞች፣ ከባቢሎናውያን ወረራ ያመለጡ ይመስላል፤ ሆኖም ቤቴል፣ የባቢሎን ሰራዊት ለቆ የፋርስ ሰራዊት በእግሩ ሲተካ ወድማለች። በዕዝራ ዘመን በዚሁ ስፍራ አንዲት አነስተኛ መንደር እንደ ተገኘች የታሪክ ቅርሶች ጥናት ያረጋግጣል።

*2፥31፤* ቍ 7 ይመ።

2፥33 *የሎድ፤* የአሁኗ ልዳ ናት።

*2፥35 የሴናዓ፤* ከምርኮ ከተመለሱት ሰዎች ከፍተኛው ቍጥር (3630) ከሴናዓ ጋር የተያያዘ ነው፤ ይህ ቍጥር በነህ 7፥38 ላይ 3930 ተብሎ ተመዝግቦአል። ስሙ እንደሚያመለክተው፣ እነዚህ ሰዎች ከአንድ ቦታ የመጡ ወይም ከአንድ ቤተ ሰብ የተገኙ ሳይሆኑ፣ በማኅበራዊ ኑሮ ደረጃ ዝቅተኛ ስፍራ የነበራቸው ሰዎች ሊሆኑ ይችላሉ።

*2፥36-39፤* አራት የካህናት ጐሣዎች የተጠቀሱበት ክፍል ነው፤ ቍጥራቸውም 4289 ሲሆን፣ ከጠቅላላው ሕዝብ አንድ ዐሥረ

| | |
|---|---|
| [37]የኢሜር ዘሮች | 1,052 |
| [38]የፋስኮር ዘሮች | 1,247 |
| [39]የካሪም ዘሮች | 1,017 |

[40]ሌዋውያኑ፦

| | |
|---|---|
| በሆዳይዋ በኩል የኢያሱና የቀድምኤል ዘሮች | 74 |

[41]መዘምራኑ፦

| | |
|---|---|
| የአሳፍ ዘሮች | 128 |

[42]የቤተ መቅደሱ በረኞች፦

| | |
|---|---|
| የሰሎም፣ የአጤር፣ የጤልሞን፣ የዓቁብ፣ የሐጢጣና የሶባይ ዘሮች | 139 |

[43]የቤተ መቅደሱ አገልጋዮች፦
የሲሐ፣ የሐሡፋና የጠብዖት ዘሮች፤
[44]የኬራስ፣ የሲዓ፣ የፋዶን ዘሮች፤
[45]የልባና፣ የአጋባ፣ የዓቁብ ዘሮች፤
[46]የአጋብ፣ የሰምላይ፣ የሐናን ዘሮች፤
[47]የጊዴል፣ የጋሐር፣ የራያ ዘሮች፤
[48]የረአሶን፣ የኔቆዳ፣ የጋሴም ዘሮች፤
[49]የዖዛ፣ የፋሴሐ፣ የቤሳይ ዘሮች፤
[50]የአስና፣ የምዑናውያን፣ የንፉሲም ዘሮች፤
[51]የበቅቡቅ፣ የሐቁፋ፣ የሐርሑር ዘሮች፤
[52]የበስሎት፣ የምሒዳ፣ የሐርሳ ዘሮች፤
[53]የበርቆስ፣ የሲሣራ፣ የቴማ ዘሮች፤
[54]የንስያና የሐጢፋ ዘሮች፤

2፥37 1ዜና24፥14
2፥38 1ዜና9፥12
2፥39 1ዜና24፥8
2፥40 ዘኍ29፥34፤ ዘኍ3፥9፤ዘዳ18፥6-7፤ 1ዜና16፥4፤ዕዝ7፥7፤ 3፥9፤8፥15፤ነህ12፥24
2፥41 1ዜና15፥16
2፥42 1ሳሙ3፥15፤ 1ዜና9፥17
2፥43 1ዜና9፥2፤ ነህ11፥21
2፥58 1ዜና9፥2
2፥59 ዘኍ1፥18
2፥61 2ሳሙ17፥27
2፥62 ዘኍ3፥10፤ 16፥39-40
2፥63 ዘፀ28፥30፤ ዘሌ2፥3፡10
2፥65 2ሳሙ19፥35

[55]የሰሎሞን አገልጋዮች ዘሮች፦
የሶጣይ፣ የሶፌሬት፣ የፍሩዳ ዘሮች፤
[56]የየዕላ፣ የደርቆን፣ የጊዴል ዘሮች፤
[57]የሰፋጥያስ፣ የሐጢል፣ የፌክራት፣የሐጺ በይም፣ የአሚ ዘሮች፤

| | |
|---|---|
| [58]የቤተ መቅደሱ አገልጋዮችና የሰሎሞን አገልጋዮች ዘሮች | 392 |

[59]ከዚህ የሚከተሉት ደግሞ ከቴልሜላ፣ ከቴላሬሳ፣ ከክሩብ፣ ከአዳንና ከኢሜር ከተሞች የመጡ ናቸው፤ ነገር ግን ቤተ ሰቦቻቸው የእስ ራኤል ዘር መሆናቸውን ማስረዳት አልቻሉም፤

| | |
|---|---|
| [60]የደላያ፣ የጦብያና የኔቆዳ፣ ዘሮች | 652 |

[61]ከካህናቱ መካከል የኤብያ፣ የአቆስና የቤ ርዜሊ ዘሮች፤ ቤርዜሊ በዚህ ስም ሊጠራ የቻ ለው የገለዓዳዊውን የቤርዜሊን ልጅ አግብቶ ስለ ነበር ነው::

[62]እነዚህ በትውልድ መዝገቡ ውስጥ የቤተ ሰባቸውን ዝርዝር ፈለጉ፤ ነገር ግን ማግኘት አል ቻሉም፤ ስለዚህ እንዳልነጹ ተቈጥረው፣ ከክ ህነት አገልግሎት ተገለሉ:: [63]አገረ ገዥውም በኡሪምና በቱሚም እግዚአብሔርን የሚጠይቅ ካህን እስኪነሣ ድረስ፣ እጅግ ከተቀደሰው ምግብ እንዳይበሉ አዘዛቸው::

| | |
|---|---|
| [64]ከምርኮ የተመለሱት ሰዎች ብዛት | 42,360 |

ነበረ፤ [65]ይህም 7,337 ከሚሆኑት ከወንዶችና ከሴቶች አገልጋዮቻቸው በተጨማሪ ነው፤ 200

ኛውን ይይዛሉ::

2፥40 *ሌዋውያኑም*፤ በዚሌዋውያን መግቢያ ላይ "አስያየሙ" የሚለውን ይመ:: ከምርኮ የተመለሱት ሌዋውያን በቍጥር ከሌላው በጣም አነስተኛ ናቸው (ከ8፥15 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ሌዋውያኑ በቤተ መቅደሱ ውስጥ የነበራቸው የሥራ ድርሻ ተራ ስለነበር፣ አብዛኞቹ በምርኮ አገር የነበረውን ኑሮ ወደውት እዚያው መቅረቱን ሳይመርጡ አልቀሩም::

2፥41 *የአሳፍ፡ ዳዊት* ለቤተ መቅደሱ መዘምራን አለቃ አድርጎ ከሾማቸው (1ዜና 25፥1፤ 2ዜና 5፥12፤ 35፥15) ከሦስቱ ሌዋውያን አንዱ ነው፤ የመዘምራኑ ተግባር በ1ዜና 15፥16-24 ላይ ተዘርዝሮአል::

*2፥42 በረኞች*፤ በአብዛኛው ሌዋውያን ናቸው (1ዜና 9፥26፤ 2ዜና 23፥4፤ 35፥15፤ ነህ 12፥25፤ 13፥22):: በዕዝራና በነህምያ መጻሕፍት ውስጥ 16 ጊዜ፣ በመጻሕፍተ ዜና መዋዕል ደግሞ 19 ጊዜ ተጠቅሰዋል:: ዋናው ሥራቸው የቤተ መቅደሱን በርና የቅጥር ግቢውን መግቢያ መክፈትና መዝጋት (1ዜና 9፥17-27) እንዲሁም ሌሎች ተራ ሥራዎችን ማከናወን ነበር (1ዜና 9፥28-32፤ 2ዜና 31፥14)::

*2፥43-57*፤ የቤተ መቅደሱ አገልጋዮችና የሰሎሞን አገልጋዮች ዝርያዎች ጠቅላላ ቍጥር 392 ነበር (ቍ 58)፤ ይህም ከመዘምራኑና ከበር ጠባቂዎቹ ሌዋውያን አጠቃላይ ቍጥር (ቍ 40-42) ይበልጣል::

2፥46 *የሐናን*፤ የስሙ ትርጕም፣ "(እግዚአብሔር) ቸር ነው" ማለት ሲሆን፣ በብሉይ ኪዳን "ቸር መሆን" የሚለው ግሥና ከዚሁ የተገኙት ቃላት ለብዙ ሰዎች የተጸውዖ ስም ሆነዋል:: ለምሳሌ ዮሐናን ("እግዚአብሔር ቸር ነው"፤ 8፥12 ይመ) አንዱ ሲሆን፣ በአ ማርኛ "ዮሐንስ" የሚለው ስም ከዚሁ የመጣ ነው::

2፥51 *በቅቡቅ*፤ የስሙ ትርጕም "ገምቦ" ማለት ሲሆን፣ ለወፍራምና ለቦርጫም ሰው የተሰጠ የቅጽል ስም ሳይሆን አይቀርም:: በኤር 19፥1፡10 ላይ "ገምቦ" ተብሎ ከተተረጐመው ጋር ያነጻ ጽሩ፤ በኤር 19፥7 ላይ "አፈርሳለሁ" ተብሎ የተተረጐመው የዕብ ራይስጥ ቃል ከዚሁ (ከበቅቡቅ) ጋር አንድ ነው::

2፥53 *የበርቆስ*፤ "የቆስ ልጅ" ማለት ነው (ወይም የኤዶ ማውያን ጣዖት "ቈስ" ነው::)

2፥55-58፤ *የሰሎሞን አገልጋዮች ዘሮች*፤ ይህ አባባል የሚገኘው በዚህ ክፍልና በነህ 7፥57፡60፤ 11፥3 ላይ ብቻ ነው:: እነዚህ ሰዎች ምናልባት ንጉሥ ሰሎሞን ገባሮች ያደረጋቸው የከነዓናውያን ዝርያዎች ሳይሆኑ አይቀሩም (1ነገ 9፥20-21)::

2፥55 *የሶፌሬት*፤ ምናልባት፣ "የጸሐፊው ተግባር" ማለት ሊሆን ይችላል፤ በአንድ ወቅት ለጸሐፊዎች የተሰጠ የማዕረግ ስም ሳይሆን አይቀርም::

*2፥59-63*፤ የዘር ሐረጋቸውን በትክክል መቍጠር ያልቻሉ ግለሰቦች ናቸው::

2፥59 *ከቴልሜላ*፤ የስሙ ትርጕም፣ "የጨው ቍልል" ማለት ነው፤ ምናልባት ጨው የተነሰነሰበት ስፍራ ሊሆን ይችላል (መሳ 9፥45 እና ማብ ይመ):: "ቴል" የሚለው የዕብራይስጥ ቃል ለተቈለለ ነገር የሚውል ሲሆን በከተማ ፍርስራሽ የሚፈጠረውን ስፍራ ያመለክታል (የኢሱ 11፥13 ማብ ይመ):: የተጋዙት አይሁዳውያን ምርኮኞች እንዲሰፍሩ የተደረገው በኮቦር ወንዝ አካባቢ ነበር (ሕዝ 1፥1)፤ ይህ ስፍራ የሚገኘው በደቡብ መስጴጦምያ የምትገኝ ምሽግ በነበረችው በኔፑር ከተማ ሳይሆን አይቀርም:: የአይሁድ ሕዝብ እንዲሰፍር የተደረገው፣ ባቢሎናውያን የፍርስራሽ ክምር ባደረጓቸው ከተሞች ሊሆን ይችላል:: *ከተሞች*፤ ባቢሎናውያን የአይሁድን ሕዝብ ያሰፈሩ ባቸው በመስጴጦምያ የሚገኙ ቦታዎች ናቸው::

2፥61 *ቤርዜሊ*፤ የስሙ ትርጕም፣ "የብረት ሰው" ማለት ነው:: በዚህ ስም ስለተጠሩ ሰዎች 2ሳሙ 17፥27-29፤ 19፥31-39፤ 1ነገ 2፥7 ይመ::

2፥63 *አገረ ገዥውም*፤ ምናልባት ሰሳብሳርን ወይም ዘሩ ባቤልን ሊሆን ይችላል (የ1፥8 ማብ ይመ):: *ኡሪምና ቱሚም*፤ የዘፀ 28፥30 ማብ ይመ::

2፥64 *42360*፤ ድምሩ ከተሰጡት ከሌሎቹ ቍጥሮች በላይ ነው፤

| ምድብ | ዕዝራ | ነህምያ | 1ኢስድራስ |
|---|---|---|---|
| የእስራኤል ሰዎች | 24,144 | 25,406 | 25,947 |
| ካህናት | 4,289 | 4,289 | 5,288 |
| ሌዋውያን፣ መዘምራን፣ በር ጠባቂዎች፣ የቤተ መቅደስ አገልጋዮች፣ የሰሎሞን አገልጋዮች ዘሮች | 392 | 392 | 372 |
| ትውልዳቸው የማይታወቅ ሰዎች | 652 | 642 | 652 |
| ድምር | 29,818 | 31,089 | 32,600 |

ከ10,000-12,000 የሚደርሰው ይህ ልዩነት እንዴት እንደመጣ መናገር አስቸጋሪ ነው:: ቍጥሩ የሚያመለክተው ስማቸው ያልተጠቀሰውን ከ10,000-12,000 የሚደርሱትን ሴቶችና ሕፃናት ሊሆን ይችላል፤ ከዚሁ በተጨማሪ በቍ 61-63 ላይ የተጠቀሱትንና ትውልዳቸው በውል የማይታ ወቀውን ካህናት እንደሚጨምር ምንም ጥርጥር የለውም:: አንዳንድ ሊቃው ንት እንደሚናገሩት ቍጥራቸው በግልጽ የተጠቀሰው፣ ከይሁዳና ከብንያም ወገን የሆኑት ተመላሾች ሲሆኑ፣ የቀሩት ደግሞ ከሌሎች ወገን ናቸው::

*2፥65 ከወንዶችና ከሴቶች አገልጋዮቻቸው*፤ የአገልጋዮቹ ቍጥር ከሌሎቹ ጋር ሲነጻጸር አንድ ለስድስት ይሆናል፤ ይህም ከፍተኛ

ወንድና ሴት ዘማሪዎችም ነበሯቸው። [66]736 ፈረሶች፣ 245 በቅሎዎች፣ [67]435 ግመሎችና 6,720 አህዮች ነበሯቸው።

[68]በኢየሩሳሌም ወደሚገኘው ወደ እግዚአብሔር ቤት በደረሱ ጊዜ፣ አንዳንድ የቤተ ሰብ መሪዎች፣ በቀድሞው ቦታ እንደ ገና ለሚሠራው የእግዚአብሔር ቤት በበጎ ፈቃድ ስጦታ አደረጉ። [69]እንደየችሎታቸውም 61,000 የወርቅ ዳሪክ[ሠ]፣ 5,000 ምናን[ረ] ብር፣ 100 ልብሰ ተክህኖ ለግምጃ ቤቱ ሰጡ።

[70]ካህናቱ፣ ሌዋውያኑ፣ መዘምራኑ፣ በር ጠባቂዎቹና የቤተ መቅደስ አገልጋዮቹ፣ ከሌሎች ሰዎች ጋር በየራሳቸው ከተሞች ሰፈሩ፤ የቀሩት እስራኤላውያንም በየከተሞቻቸው ተቀመጡ።

## መሠዊያው እንደ ገና ተሠራ

3 ሰባተኛው ወር በደረሰ ጊዜ፣ እስራኤላውያን በየከተሞቻቸው ሳሉ፣ ሕዝቡ እንደ አንድ ሰው ሆነው በኢየሩሳሌም ተሰበሰቡ። [2]ከዚያም የኢዮሴዴቅ ልጅ ኢያሱና ካህናት ዘመዶቹ እንዲሁም የሰላትያል ልጅ ዘሩባቤልና የሥራ ባልደረቦቹ፣ በእግዚአብሔር ሰው በሙሴ ሕግ በተጻፈው መሠረት የሚቃጠል መሥዋዕት ለማቅረብ፣ የእስራኤልን አምላክ መሠዊያ መሥራት ጀመሩ። [3]በዙሪያቸው ካሉት አሕዛብ የተነሣ ፍርሀት ቢያድርባቸውም፣ መሠዊያውን በቀድሞው መሠረት ላይ ሠሩ፤ በመሠዊያውም ላይ ጠዋትና ማታ የሚቀርበውን የሚቃጠል መሥዋዕት ለእግዚአብሔር አቀረቡ። [4]ከዚያም ለእያንዳንዱ ቀን እንደ ታዘዘው፣ በሚያስፈልገው ቍጥር ልክ የሚቃጠል መሥዋዕት በማቅረብ የዳስ በዓልን በተጻፈው መሠረት አከበሩ። [5]ከዚያም በኋላ መደበኛውን የሚቃጠል መሥዋዕት፣ የወር መባቻን መሥዋዕት፣ በተቀደሱት የእግዚአብሔር በዓላት የሚቀርበውን መሥዋዕትና በበጎ ፈቃድ ለእግዚአብሔር የሚሰጠውን መባ አቀረቡ። [6]የእግዚአብሔር ቤት መቅደስ መሠረት ገና ያልተጣለ ቢሆንም፣ በሰባተኛው ወር በመጀመሪያው ቀን ለእግዚአብሔር የሚቃጠል መሥዋዕት አቀረቡ።

## ቤተ መቅደሱ እንደ ገና ተሠራ

[7]ከዚያም ለድንጋይ ጠራቢዎችና ለዐናጢዎች ገንዘብ ሰጡ፤ ከፋርስ ንጉሥ ከቂሮስ በተፈቀደው መሠረት የዝግባ ዛፎች ከሊባኖስ ወደ ኢዮጴ በባሕር እንዲያመጡላቸው፣ ለሲዶናና ለጢሮስ ሰዎችም ምግብ፣ መጠጥና ዘይት ሰጡ።

[8]ኢየሩሳሌም ወደሚገኘው ወደ እግዚአብሔር ቤት በደረሱ በሁለተኛው ዓመት በሁለተኛው ወር፣ የሰላትያል ልጅ ዘሩባቤልና የኢዮሴዴቅ ልጅ ኢያሱ እንዲሁም የቀሩት ወንድሞቻቸው (ካህናቱ፣ ሌዋውያኑ፣ ከምርኮ ወደ ኢየሩሳሌም የተመለሱት ሁሉ) ሃያ ዓመትና ከዚያም በላይ የሆናቸው ሌዋውያን የእግዚአብሔርን ቤት ሕንጻ ሥራ እንዲቈጣጠሩ ሾሟቸው፤ ሥራውንም ጀመሩ። [9]ኢያሱ፣ ወንዶች ልጆቹና ወንድሞቹ፣ የዮሑዳያ[ሰ] ዘሮች ቀድምኤልና ወንዶች ልጆቹ፣ የኤንሐዳድ ወንዶች ልጆች፣ ልጆቻቸውና ወንድሞቻቸው፣ ሌዋውያንም ሁሉ የእግዚአብሔርን ቤት የሚሠሩትን ሰዎች ለመቈጣጠር በአንድ ላይ ሆኑ።

[10]ግንበኞቹ የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ መሠረት በጣሉ ጊዜ፣ ካህናቱ ልብሰ ተክህኖአቸውን ለብሰውና መለከታቸውን ይዘው፣ ሌዋውያኑ የአሳፍ ልጆች ደግሞ ጸናጽል ይዘው፣ በእስራ

2፥66 ኢሳ66፥20
2፥68 ዘፀ25፥2
2፥70 ቍ1፤ 1ዜና9፥2፤ ነህ11፥3-4
3፥1 ዘሌ23፥24፤ ነህ7፥73
3፥2 ዘፀ20፥24፤ ዘዳ12፥5-6፤1ዜና3፥17፤ ዕዝ2፥2፤ሐጌ1፥1፤ ዘካ6፥11
3፥3 ዘፀ29፥39፤ ዘኍ28፥1-8፤ዕዝ4፥4፤ ዳን9፥25
3፥4 ዘፀ23፥16፤ ዘኍ29፥12-38፤ ነህ8፥14-18፤ ዘካ14፥16-19
3፥5 ዘሌ23፥1-44፤ ዘኍ28፥14፤29፥39፤ ቈላ2፥16
3፥7 1ዜና14፥1፤ 22፥15፤ዕዝ1፥2-4፤ ኢሳ35፥2፤60፥13
3፥8 ዘኍ4፥3፤ 1ዜና6፥1፤ዘካ4፥9
3፥9 ዕዝ2፥40
3፥10 ዘኍ10፥2፤ 2ሳሙ6፥5፤1ዜና6፥31፤ 16፥6፤25፥1፤2ዜና5፥13፤ ዕዝ5፥16፤6፥3፤ነህ12፥35፤ ሐጌ2፥15፤ዘካ6፥12

[ሠ]69 500 ኪሎ ግራም ያህል ነው።
[ረ]69 2.9 ሜትሪክ ቶን ያህል ነው።
[ሰ]9 ዕብራይስጡ፣ ይሁዳ ይላል፤ ምናልባት ከዮሑዳያ ጋር ተመሳሳይ ነው።

አንዝ ነው፤ ብዙ አገልጋዮች ከጌቶቻቸው ጋር መመለሳቸው የሚያመለክተው የአይሁድ ሕዝቦች ለአገልጋዮቻቸው መልካም ሰዎች መሆናቸውን ነው። *ዘማሪዎች*፤ እዚህ ዝርዝር ውስጥ የተጠቀሱት ወንዶችና ሴቶች ዘማሪዎች ከክህነት አገልግሎት ውጭ፣ በሰርግና በቀብር ሥነ ሥርዐት ላይ (2ዜና 35፥25) የሚዘፍኑና የሚያቀነቅኑ (2ዜና 35፥25) ሊሆኑ ይችላሉ። እነዚህም በቍ 41 ላይ ከተጠቀሱት የቤተ መቅደሱ መዘምራን የተለዩ ናቸው፤ የቤተ መቅደሱ መዘምራን ወንዶች ብቻ ናቸው።

2፥66 *ፈረሶች*፤ ንጉሥ ቂሮስ ለአይሁድ መሳፍንትና መኳንንት የሰጣቸው ሳይሆኑ አይቀሩም። *በቅሎዎች*፤ በእነዚህ እንስሳት የሚጠቀሙት አብዛኛውን ጊዜ ንጉሣውያን ቤተ ሰቦችና ባለጠጎች ብቻ ነበሩ (1ነገ 1፥33፤ ኢሳ 66፥20)።

2፥67 *አህዮች*፤ ዕቃን ለመጫን የሚጠቅሙ ሲሆን፣ ልጆችና ሴቶችም ይቀመጡባቸዋል። በጎችና ፍየሎች እንዲሁም ሌሎች የቀንድ ከብቶች አልተጠቀሱም፤ ጕዞውን ስለሚያስተጓጉሉ ትተዋቸው ሊሆን ይችላል።

*2፥69*፤ የዚህ ክፍል ተጓዳኝ (ነህ 7፥70-72) በዕዝራ ላይ ከተገለጸው ይልቅ የተሟላ መግለጫ አለው። በዕዝራ መጽሐፍ ስጦታዎቹን ያቀረቡት የቤተ ሰብ አለቆች ናቸው (ቍ 68)፤ በነህምያ መጽሐፍ ግን ስጦታዎቹን ያበረከቱት አገረ ገዢው፣ የቤተ ሰብ አለቆችና የተቀሩት ሰዎች በሙሉ ናቸው። *ዳሪክ* ከጥሬ ብር የተሠራ የግሪኮች ሳንቲም ነበር። አንዳንዶች ግን እዚህ ላይ የተጠቀሰው የግሪኩ ሳይሆን፣ የፋርሱ የወርቅ ሳንቲም ነው ይላሉ። *ምናን* ለመጀመሪያ ጊዜ በሥራ ላይ የዋለው በመስጴጦምያ ነው። 60 ሰቅል አንድ ምናን፣ 60 ምናን አንድ ታላንት ነበር። አንድ ሰቅል የአንድ ወር አማካይ ደመወዝ ነበር፤ ስለዚህ አንድ ምናን የአምስት ዓመት ደመወዝ፣ አንድ ታላንት ደግሞ የሦስት መቶ ዓመት ደመወዝ ነው።

*2፥70*፤ በኋላ ግን ነህምያ (11፥1-2)በኢየሩሳሌም የሚኖረውን ሕዝብ ቍጥር ለመጨመር ሲል ሌሎች ሰዎችን በዕጣ ለመውሰድ ተገዶ ነበር።

3፥1 *ሰባተኛው ወር*፤ በወርሃ ጢሽሪ (ከመስከረም - ጥቅምት) ማለትም ምርኮኞቹ ይሁዳ ከደረሱ ከሦስት ወር በኋላ ነው (በ537 ዓ.ቅ.ክ)። ጢሽሪ በአይሁድ እጅግ የተቀደሱ በዓላት ከሚከበርባቸው ወራት አንዱ ነው (ዘሌ 23፥23-43 እና ማብ ይመ)።

3፥2 *ኢያሱ ... ዘሩባቤል*፤ ከወቅቱ ሁኔታ የተነሣ ከሕዝቡ መሪ ይልቅ ካህኑ ቅድሚያ አግኝቶአል (ከ3፥8፤4፥3፤5፥2፤ ከሐጌ 1፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥4 *የዳስን በዓል*፤ ዘሌ 23፥33 – 43 እና ማብ ይመ።

3፥5 *የወር መባቻ*፤ የ1ሳሙ 20፥5 ማብ ይመ። *በተቀደሱት ... በዓላት*፤ የዘሌ 23፥2 ማብ ይመ። *በበጎ ፈቃድ ... የሚቀርበውን*፤ የ1፥4 ማብ ይመ። እዚህ ላይ ከቤተ መቅደሱ መሠራት አስቀድሞ መሥዋዕት የቀረበ መሆኑን ማስተዋል ያስፈልጋል።

3፥7 *የዝግባ ግንድ*፤ ቤተ መቅደሱ መጀመሪያ ሲሠራ እንዳደረጉት ሁሉ፣ የፊንቄ ሰዎች አሁንም ዕንጨትና ሠራተኛ በመላክ ተባብረዋል (1ነገ 5፥6-12)።

3፥8 *በሁለተኛው ዓመት*፤ የአይሁድ ሕዝብ ወደ ምድራቸው የተመለሱት በበልግ ወራት በ537 ዓ.ቅ.ክ አካባቢ ስለ ነበር፣ የተባለው ሁለተኛ ዓመት፣ በ536 ዓ.ቅ.ክ በበልግ ወራት ውስጥ ማለት ነው። *በሁለተኛው ወር*፤ ንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደሱን ማሠራት ከጀመረበት ወር (1ነገ 6፥1) ጋር አንድ ነው (ሚያዝያ - ግንቦት)። *ሀያ ዓመት*፤ በቀድሞ ዘመን ሌዋውያን አገልግሎት የሚጀምሩበት ዝቅተኛው ዕድሜ 30 ዓመት (ዘኍ 4፥3) ወይም 25 ዓመት (ዘኍ 8፥24) ነበር፤ በኋላ ግን ወደ 20 ዓመት ዝቅ ብሎአል (1ዜና 23፥24፡27፤ 2ዜና 31፥17)፤ ይህ የሆነው ሌዋውያኑ በቍጥር አነስተኛ ስለነበሩ ሊሆን ይችላል።

3፥10 *መለከታቸውን*፤ ከብር ነጥሮ የተሠራ ነው (ዘኍ 10፥2 እና ማብ ይመ)። ዮሴፍ ወልደ ኩሪዮን ስለመለከት ሲናገር "ርዝመቱ ከአንድ ክንድ ትንሽ የሚያንስ፣ እንደ መቃ ውስጠ ክፍት፣ ከዋሽንት ትንሽ የሚወፍር ነው" ይላል። መለከት ሁልጊዜ የሚነፋው በካህናት ነው፤ ይሁንና በኢዮአስ ሥርዐተ ንግሥ ጊዜ ብቻ መለከቶቹን ሌሎች ሰዎች ነፍተዋቸዋል (2ነገ 11፥14፤ 2ዜና 23፥13)። መለከት

ኤል ንጉሥ በዳዊት መመሪያ መሠረት እግዚአ ብሔርን ለመወደስ ስፍራቸውን ያዙ። [11]በውዳ ሴና በምስጋናም ለእግዚአብሔር እንዲህ ሲሉ ዘመሩ፤

"ቸር ነውና፤ ለእስራኤልም ምሕረቱ ለዘላ ለም ነውና።" የእግዚአብሔር ቤት መሠረት ስለ ተጣለ፣ ሕዝቡ ሁሉ በታላቅ ድምፅ እልል እያሉ፣ ለእግዚአብሔር ምስጋና አቀረቡ። [12]የቀድሞ ውን ቤተ መቅደስ ያዩ በዕድሜ የሸመገሉ ብዙ ካህናት፣ ሌዋውያንና የቤተ ሰብ አለቆች የዚህ ቤተ መቅደስ መሠረት ሲጣል ባዩ ጊዜ፣ ድምፃ ቸውን ከፍ አድርገው አለቀሱ፤ ሌሎቹ ግን የደ ስታ ጩኸት አሰሙ። [13]የሕዝቡ ጩኸት ድብ ልቅልቅ ያለ ስለ ነበር፣ የደስታውን እልልታ ከልቅሶው ጩኸት መለየት የሚችል ማንም አልነበረም፤ ድምፁም ከሩቅ ይሰማ ነበር።

3፥11 ኢሱ6፥5:10፤ 1ዜና16፥34:41፤ 2ዜና7፥3፤መዝ30፥5፤ 107፥1፤118፥1፤138፥8፤ ሐጌ2፥18፤ዘካ4፥9፤8፥9
3፥12 ኤር31፥9፤ 50፥4፤ሐጌ2፥3:9
3፥13 አዩ8፥21፤ 33፥26፤ መዝ27፥6፤ 42፥4፤ኢሳ16፥9፤ ኤር48፥33
4፥1 ነህ2፥20
4፥2 2ነገ17፥24:41

## ቤተ መቅደሱ እንዳይሠራ የተነሣ ተቃውሞ

4 የይሁዳና የብንያም ጠላቶች ከምርኮ የተ መለሱት ሰዎች የእስራኤልን አምላክ የእግዚ አብሔርን ቤተ መቅደስ በመሥራት ላይ መሆናቸውን ሲሰሙ፣ [2]ወደ ዘሩባቤልና ወደ ቤተ ሰቡ አለቆች መጥተው፣ "እኛም እንደ እናንተ አምላካችሁን የምንፈልግ ነን፤ የአሦር ንጉሥ አስ ራዶን ወደዚህ ካመጣን ጊዜ ጀምሮ ለእርሱ ሰንሠዋ ለት ቈይተናል፤ ስለዚህ አብረን ከእናንተ ጋር እንሥራ" አሏቸው።

አብዛኛውን ጊዜ የሚነፋው በደስታ ጊዜ ብቻ ነው፤ ይኸውም እዚህ ላይ እንደ ተገለጸው፣ የኢየሩሳሌም ቅጥር እንደ ገና ተሠርቶ ባለቀ ጊዜ፣ በምረቃው ሥርዐት ላይ (ነህ 12፥35፤ ከ2ዜና 5፥13፤ ከመዝ 98፥6 ጋር ያነጻጽሩ)እንዲነፋ ተደርጓል። ጸናጽል፤ ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ ዐሥራ ሦስት ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል፤ እዚህ ላይ ከተጠቀሰውና ከነህ 12፥27 በስተቀር ሌሎቹ በሙሉ የሚገኙት በዜና መዋዕል መጻሕፍት ውስጥ ነው።

*3፥11 ዘመሩ፤* እየተቀባበሉ ዘመሩ ማለት ሊሆን ይችላል፤ ምናልባት መዘምራኑ ሁለት ቦታ ተከፍለው አንዱ አንዱን ክፍል ሲዘምር፣ ሌላው ደግሞ ሌላውን ክፍል እየተቀባበሉ እንደሚዘምሩ ያመለክታል። *ቸር ነውና ...ምሕረቱ ለዘላለም ነውና፤* ለምሳሌ 1ዜና 16፥34፤ 2ዜና 5፥13፤ መዝ 100፥5 ይመ። *እልል እያሉ፤* ኢሱ 6፥5:20፤ 1ሳሙ 4፥5፤ መዝ 95፥ 1 ይመ።

3፥13 *የደስታውን እልልታ ከልቅሶው ጩኸት፤* የእስራኤል ሕዝብ ስሜቱን በደስታና በእልልታ መግለጽ የተለመደ ነበር (10፥1፤ ነህ 1፥4፤ 8፥9)፤ ፍርድ እንዲመጣባቸው የፈቀደው አምላክ አሁን ደግሞ ወደ ምድራቸው መለሳቸው፤ ያቀዱትንም እንዲፈጽሙ ረዳቸው። በአንድ የባቢሎን የማእዘን ድንጋይ ላይ እንዲህ የሚል ቃል ተጽፎ ይገኛል "ሥራዬን እያለቀስሁ ጀመርሁ፣ የጨረስሁት ግን በደስታ ነው"፤ ከመዝ 126፥5-6 ጋር ያነጻጽሩ።

*4፥1-23* ይህ ክፍል የአይሁድን ሕዝብ ዕቅድና ጥረት ለማ ሰናከል ስለ ተደረገው ሙከራ ባጭሩ ይናገራል፤ ከቍ 1-5 ባለው ክፍል ጸሓፊው፣ በቂሮስ ዘመነ መንግሥት (ከ559-530 ዓ.ቅ.ክ) የተከናወኑትን ድርጊቶች ይገልጻል፤ በቍ 6 ላይ በጠረክሲስ ዘመነ መንግሥት (486-465 ዓ.ቅ.ክ) እንዲሁም ከቍ 7-23 ባለው ክፍል በቀዳማዊ አርጤክስስ ዘመነ መንግሥት (ከ465-424 ዓ.ቅ.ክ) የተፈጸመውን ድርጊት ያወሳል። ከዚያም ቍ 24 ላይ ወደ ቀዳማዊ ዳርዮስ ዘመነ መንግሥት (522-486 ዓ.ቅ.ክ) ይመለሳል፤ የቤተ መቅደሱ ሥራ የተፈጸመው በዚሁ ንጉሥ ዘመነ መንግሥት ነበር (5፥1-2፤ 6፥13-15፤ ትንቢተ ሐጌ፤ ዘካ 1፥1-17፤ 4፥9 ይመ)።

4፥1 *የይሁዳና የብንያም፤* የ1፥5፤ የ1ነገ 12፥21 ማብ ይመ፤ *ጠላቶች፤* "ከእናንተ ጋር እንሥራ" (ቍ 2) ያሏቸው ሰዎች የሰማርያ ሰዎች ናቸው።

*4፥2፤* የሰማርያ መንግሥት በ722-721 ዓ.ቅ.ክ ላይ ከወደቀ በኋላ፣ የአሦር ነገሥታት የመስጴጦምያንና የሶርያን ሰዎች ወደ አገ ራቸው ያፈልሱ ነበር። እነዚህ ሰዎች የሚያመልኩት የራሳቸው

## የዘሩባቤል ቤተመቅደስ




ሁለተኛው ቤተ መቅደስ የመጀመሪያው በባቢሎናውያን ከፈረሰ ግማሽ ምዕተ ዓመት በኋላ በ536 ዓ.ቅ.ክ በሰሎሞን ቤተ መቅደስ መሠረት ላይ መሠራት ተጀመረ። የቀድሞውን ቤተ መቅደስ ያስታወሱ ሰዎች ከአሁኑ ጋር በማነጻጸር አለቀሱ (ዕዝ 3:12)። በፋርስ ንጉሥ በዳርዮስ (522 - 486) በ6ኛው ዓመት በ516 ተጠናቀቀ።

የሥነ ጥንት ማስረጃዎች እንደሚያረጋግጡት በፋርስ ዘመን በፍልስጥኤም ምድር ከቁሳዊ ነገሮች ባሕል አኳያ የበለጸገ አልነበረም። በኋላም በላይኛው የግብፅ ምድር የተገኙ የአራማይክ መዛግብት አይሁዶች የአምልኮ ስፍራ ለመገን ባት ከመንግሥት ፈቃድ ያገኙበትን ሂደትና በዚህ ጊዜ የነበሩትን የተለያዩ ጠላቶች ይገልጻሉ።

ስለ ቤተመቅደሱና ስለ ግንባታው ብዙ የሚታወቅ የለም። በጊዜው ከነበሩ ጥቂት ሕንጻዎች በሶኪሶ ያለው የፋርስ ቤተ መንግሥትና በኢራቅ ኤልአሚር የነበረው ቶቢያድ በሕንጻ ቴክኒክ የሚጠቀሱ ናቸው።

በ586 ዓ.ቅ.ክ. እና በ70 ዓ.ም. እንደ ወደሙት ታላላቅ ሕንጻዎች በዘሩባቤል የተጀመረው ቤተ መቅደስ ያለ ምንም አስከፊ ውድመት ቀስ በቀስ በረጅም ጊዜ ውስጥ ታድሷል። በኋላም በሄሮድስ አስደናቂ ጎ ን ጸ ሙሉ በሙሉ ተተክቷል/ተለውጧል።

ያደረጉትም መርዶክዮስን ስለ ፈሩ ነበር:: [4]መርዶክዮስ በቤተ መንግሥቱ ታዋቂ ሆነ፤ ዝናው በየአውራጃው ሁሉ ተሰማ፤ ኀይሉም እየበረታ ሄደ::

[5]ስለዚህ አይሁድ ጠላቶቻቸውን ሁሉ በሰይፍ እየመቱ ገደሏቸው፤ አጠፏቸውም፤ በሚጠሏቸውም ላይ ደስ ያሰኛቸውን አደረጉ:: [6]አይሁድ በሱሳ ግንብ አምስት መቶ ሰው ገደሉ፤ አጠፉም:: [7]ፖርሻንዳታን፣ ደልፎንን፣ አስፓታን፣ [8]ፖራታን፣ አዳልያን፣ አሪዳታን፣ [9]ፓርማሽታን፣ አሪሳይን፣ አሪዳይንና ዋይዛታንም ገደሉ፤ [10]እነዚህም የአይሁድ ጠላት የሆነው የሐመዳቱ ልጅ የሐማ ዐሥር ወንዶች ልጆች ነበሩ:: በምርኮው ላይ ግን እጃቸውን አልዘረጉም::

[11]በሱሳ ግንብ የተገደሉት ሰዎች ብዛት በዚያኑ ዕለት ለንጉሡ ተነገረው:: [12]ንጉሡም ንግሥት አስቴርን፣ "አይሁድ በሱሳ ግንብ አምስት መቶ ሰውና ዐሥሩን የሐማ ልጆች ገድለዋል፤ አጥፍተዋልም:: በተቀሩት በንጉሡ አውራጃዎችስ ምን አድርገው ይሆን? አሁንስ የምትለምኚው ምንድን ነው? ይሰጥሻል፤ የምትጠይቂውስ ምንድን ነው? ይፈቀድልሻል" አላት::

[13]አስቴርም፣ "ንጉሥን ደስ የሚያሰኘው ከሆነ፣ በሱሳ የሚኖሩ አይሁድ የዛሬውን ዐዋጅ ነገም እንዲደግሙት ፈቃድህ ይሁን፤ ዐሥሩ የሐማ ወንዶች ልጆችም ዕንጨት ላይ ይሰቀሉ" አለች::

[14]ንጉሡም ይህ እንዲሆን አዘዘ:: በሱሳ ዐዋጅ ተነገረ፤ ዐሥሩንም የሐማ ወንዶች ልጆች ሰቀሏቸው:: [15]በሱሳ የሚኖሩ አይሁድ አዳር በተባለው ወር በዐሥራ አራተኛው ቀን በአንድነት መጡ፤ በሱሳም ሦስት መቶ ሰዎች ገደሉ፤ በምርኮው ላይ ግን እጃቸውን አልዘረጉም::

[16]በዚህ ጊዜ በሌሎች በንጉሡ አውራጃዎች የሚኖሩ የተቀሩት አይሁድ ራሳቸውን ለመከላከልና ከጠላቶቻቸውም ለመገላገል ተሰበሰቡ፤ ከሚጠሏቸውም ሰባ አምስት ሺህ ገደሉ፤ በምርኮው ላይ ግን እጃቸውን አልዘረጉም:: [17]ይህ የሆነው አዳር በተባለው ወር ዐሥራ ሦስተኛ ቀን ነበር፤ በዐሥራ አራተኛው ቀን ዐረፉ፤ ዕለቱንም የተድላና የደስታ ቀን አድርገው ዋሉ::

## የፉሪም በዓል መከበር

[18]በሱሳ የሚኖሩ አይሁድ ግን በዐሥራ ሦስተኛውና በዐሥራ አራተኛው ቀን ተሰብስበው ነበር፤ ከዚያም በዐሥራ አምስተኛው ቀን ዐረፉ፤ ዕለቱንም የተድላና የደስታ ቀን አድርገው ዋሉ::

[19]በየመንደሩ የሚኖሩ የገጠር አይሁድ፣ የአዳርን ወር ዐሥራ አራተኛ ቀን የተድላና የደስታ፣ እርስ በርሳቸውም ስጦታ የሚለዋወጡበት ቀን አድርገው የሚያከብሩት ከዚሁ የተነሣ ነው::

[20]መርዶክዮስ የተፈጸሙትን እነዚህን ድርጊቶች ጻፈ፤ ደብዳቤ አዘጋጅቶም በመላው የንጉሥ አርጤክስስ አውራጃ በቅርብና በሩቅ ለሚገኙት አይሁድ ሁሉ ላከ፤ [21]የላከውም የአዳርን ወር ዐሥራ አራተኛና ዐሥራ አምስተኛ ቀን በየዐመቱ እንዲያከብሩ ነው፤ [22]የሚያከብሩበትም ምክንያት አይሁድ ከጠላቶቻቸው ዕረፍት ያገኙበት፣ ሐዘናቸው ወደ ደስታ፣ ልቅሷቸውም ወደ ክብረ በዓል የተለወጠበት ቀን ስለ ሆነ ነው:: ቀኖቹንም የተድላና የደስታ ቀኖች አድርገው፣ እርስ በርሳቸውም የምግብ ስጦታ እየተለዋወጡና ለድኾችም ስጦታ እየሰጡ እንዲያከብሩ ጻፈላቸው::

[23]ስለዚህ አይሁድ መርዶክዮስ የጻፈላቸውን ለመፈጸምና የጀመሩትን በዓል ለማክበር ተስማሙ፤ [24]ምክንያቱም የአይሁድ ሁሉ ጠላት የሆነው የአጋጋዊው የሐመዳቱ ልጅ ሐማ አይሁድን ለማጥፋት አሢሮ ነበር፤ ሊፈጃቸውና ሊያጠፋቸውም ፉር የተባለ ዕጣ ጥሎ ነበር:: [25]ሤራው በንጉሡ ዘንድ እንደ ታወቀ[a] ሐማ በአይሁድ ላይ የሸረበው ሤራ በገዛ ራሱ ላይ እንዲጠመጠም፣ እርሱና ወንዶች ልጆቹም በዕንጨት ላይ እንዲሰቀሉ የጽሑፍ ትእዛዝ አስተላለፈ:: [26]ስለዚህ እነዚህ ቀኖች ፉር ከሚለው ቃል "ፉሪም" ለመባል በቁ:: በዚህ ደብዳቤ ስለ

[a]25 ወይም፣ አስቴር በንጉሡ ፊት በመጣች ጊዜ

9፥4 ዘፀ11፥3፤ 2ሳሙ3፥1፤1ዜና11፥9፤ አስ8፥15
9፥5 ዘዳ25፥17-19፤ 1ሳሙ15፥3፤ዕዝ4፥6
9፥10 ዘፍ14፥23፤ 1ሳሙ14፥32፤15፥33፤ አስ3፥13፤5፥11፤መዝ 127፥3-5
9፥12 አስ5፥6፤7፥2
9፥13 ዘዳ21፥22-23፤አስ5፥11
9፥14 ዕዝ6፥14
9፥15 ዘፍ14፥23፤ አስ8፥11
9፥16 ዘዳ25፥19፤ 1ዜና4፥43፤አስ4፥14፤ 8፥11
9፥17 1ነገ3፥15
9፥19 አስ2፥9፤3፥7፤ ራእ11፥10
9፥22 2ነገ25፥30፤ ነህ8፥10:12፤አስ4፥14፤ መዝ30፥11-12
9፥24 ዘፀ17፥8-16፤ ዘሌ16፥8፤አስ3፥6:7
9፥25 ዘዳ21፥22-23፤ አስ7፥10፤መዝ7፥16
9፥26 አስ3፥7

*9፥5-10፤* የአይሁድ ሕዝብ "የአማሌቃውያንን ስም ከምድር ገጽ የማጥፋቱን" ተግባር ከግብ ለማድረስ ተነሥተዋል (ዘፀ17፥16፤ ዘዳ25፥17-19፤ የ3፥1-6 ማብ ይመ):: በዚህ ክፍል የተጠቀሰው ሁኔታ ከ1ሳሙ15 ጋር ተቃራኒ ነው:: ንጉሡ ምርኮ እንዲወስዱ ቢፈቅድላቸውም፣ ሕዝቡ ግን ምርኮ ከመውሰድ መቈጠቡን ጸሐፊው ደጋግሞ ገልጸአል (8፥11):: ከአምስት መቶ ዓመት በፊት፣ ንጉሥ ሳኦል ከአማሌቃውያን ጋር ጦርነት አድርጎ ምርኮ ስለ ወሰደ የንጉሥነት ሥልጣኑን አጥቶአል:: (1ሳሙ 15፥17-19)፤ በዚህ ክፍል የሚታየው ምርኮ ለመውሰድ ያለመስገብገብ ግን፤ ለመርዶክዮስ የቤተ መንግሥት ሥልጣን አስገኝቶለታል (ቊ-20-23):: ቊ-15-16 ይመ፤ ከዘፍ 14፥22-24 ጋር ያነጻጽሩ::

9፥10 *የሐማ ... ወንዶች ልጆች፤* በ5፥11 ላይ ከተጠቀሰው በመቀጠል ለሁለተኛ ጊዜ በዚህ ክፍል ስለ ሐማ ልጆች ተጠቅሶ አል::

*9፥12፤* 5፥3:6፤7፥2 ይመ::

*9፥13፤* እዚህ ላይ ሰዎችን መስቀል፣ የመግደያ መንገድ ሆኖ ሳይሆን፣ በድንን ሰቅሎ ለማሳየት ነው:: (ቊ-7-10 እና የ2፥23 ማብ ይመ)::

*9፥15-16፤* የቊ 5-10 ማብ ይመ::

9፥16:22፤ *ከጠላቶቻቸውም ለመገላገል፤* ለእስራኤል እግዚአብሔር ከገባው የዕረፍት ቃል ኪዳን ጋር፣ አብሮ የሚሄድ ነው (ዘዳ 25፥19):: ሐማ ድል መመታቱ ለአይሁድ ሕዝብ ዕረፍትን አስገኝቶአል፤ ከ1ዜና 22፥6-10፤ መዝ 95፥8-11፤ ኢሳ 32፥18፤ ዕብ 3፥11-4፥11 ጋር ያነጻጽሩ::

*9፥18-19፤* ጸሐፊው ፉሪም የሚከበረው በሁለት የተለያዩ ቀናት እንደ ነበር ያመለክታል፤ በብዙ ከተሞች በአዳር ወር በዐሥራ አራተኛው ቀን ሲከበር፣ በሱሳ የነበሩ አይሁድ ግን በዐሥራ አምስተኛው ቀን ያከብሩት ነበር:: በአሁኑ ዘመን በዐሥራ አራተኛው ቀን ያከብሩታል፤ በኢየሩሳሌም የሚከበረው ግን በዐሥራ አምስተኛው ቀን ነው::

9፥20 *መርዶክዮስ ... እነዚህን ድርጊቶች ጻፈ፤* አንዳንድ ሰዎች ከዚህ ተነሥተው መጽሐፈ አስቴርን የጻፈው መርዶክዮስ ራሱ ነው ይላሉ፤ የሚታመነው አመለካከት ግን፣ መርዶክዮስ በላካቸው ደብዳቤዎቹ ውስጥ በወቅቱ የተፈጸሙትን ድርጊቶች መዝግቦ ይዞ ነበር የሚለው ነው::

9፥22 *የምግብ ስጦታ፤* የ2፥9 ማብ ይመ፤ ከነህ 8፥10:12 ጋር ያነጻጽሩ::

9፥24:26 *ፉር፤* የ3፥7 ማብ ይመ::

ተጻፈው ሁሉ፣ ስላዩትና ስለ ደረሰባቸውም ነገር ሁሉ፣ [27]አይሁድ በታዘዘውና በተወሰነው ጊዜ እነርሱና ዘሮቻቸው፣ እነርሱን የተጠጓቸውም ሁሉ እነዚህን ሁለት ቀኖች በየዓመቱ ባለማቋረጥ እንዲያከብሩ ሥርዐት አድርገው ራሳቸው ወሰኑ። [28]እነዚህም ቀኖች በእያንዳንዱ ትውልድ፣ በእያንዳንዱ ቤተ ሰብ፣ በእያንዳንዱ አውራጃና በእያንዳንዱ ከተማ መታሰብና መከበር ይኖርባቸዋል፤ ይኸውም እነዚህ የፉሪም ቀኖች በአይሁድ ዘንድ ሳይከበሩ እንዳይቀሩ፤ መታሰቢያቸውም ከዘሮቻቸው መካከል እንዳይደመሰስ ነው።

[29]ስለዚህ የአቢካኢል ልጅ ንግሥት አስቴር ከአይሁዳዊው ከመርዶክዮስ ጋር በመሆን፣ ፉሪምን አስመልክተው ይህችን ሁለተኛዪቱን ደብዳቤ ለማጽናት በሙሉ ሥልጣን ጻፉ። [30]መርዶክዮስም የመልካም ምኞት መግለጫና ማረጋገጫ የሆነውን ደብዳቤ በአርጤክስስ ግዛት ውስጥ በሚገኙት አንድ መቶ ሃያ ሰባት አውራጃዎች ለሚኖሩት አይሁድ ሁሉ ላከ፤ [31]የላከውም አይሁዳዊው መርዶክዮስና ንግሥት አስቴር ባወጁላቸውና እንደዚሁም የጾሙንና የሰቈቃውን ጊዜ በሚመለከት ለራሳቸውና ለዘራቸው ባጸኑት ውሳኔ መሠረት እነዚህ የፉሪም ቀኖች በተወሰነላቸው ጊዜ እንዲከበሩ ነው። [32]የአስቴር ዐዋጅ ስለ ፉሪም የወጣውን ሥርዐት አጸና፤ ይህም በመዝገብ ተጻፈ።

## የመርዶክዮስ ታላቅነት

**10** ንጉሥ አርጤክስስ እስከ ባሕር ዳርቻ በሚዘልቀው ግዛቱ ሁሉ ላይ ግብር ጣለ። [2]የኀይሉና የብርታቱ ሥራ ሁሉ እንዲሁም ንጉሡ መርዶክዮስን ለዚህ የላቀ ማዕረግ እንዴት እንዳደረሰው የሚናገረው በሜዶንና በፋርስ የታሪክ መጽሐፍ የተጻፈ አይደለምን? [3]አይሁዳዊው መርዶክዮስ በማዕረግ ከንጉሡ ከአርጤክስስ ቀጥሎ ሁለተኛ፣ ከአይሁድ መካከልም ቀዳሚውን ስፍራ የያዘ ሰው ነበር፤ ለወገኖቹ መልካም በማድረጉና ለአይሁድም ሁሉ ደኅንነት የቆመ በመሆኑ፣ በብዙዎቹ አይሁድ ወገኖቹ ዘንድ እጅግ የተከበረ ነበር።

9፥29 አስ2፥15
9፥30 አስ1፥1
9፥31 አስ4፥1-3፡16
10፥1 መዝ72፥10፤ 97፥1
10፥2 ዘፍ41፥44፤ አስ2፥23፤8፥15
10፥3 ዘፍ41፥40፡ 43፤ነህ2፥10፤ኤር29፥4-7፤ዳን5፥7፤6፥3

9፥27 *እነርሱን የተጠጓቸውም ሁሉ፤* አንዳንድ ሰዎች ይህ አባባል አይሁድ ከአሕዛብ ወገን ሰዎችን ወደ ሃይማኖታቸው ያስገቡበትን ጊዜ ስለሚያመለክት፣ መጽሐፈ አስቴር መቼ እንደ ተጻፈ ለመገመት የሚረዳ ነው ይላሉ፤ በይበልጥ ግን በ8፥17 ላይ የተጠቀሱትን ሰዎች የሚያመለክት ይመስላል።

9፥31 *የጾሙንና፤* የ4፥3፡16 ግብ ይመ። ለዚህ ጾም የተለየ ቀን አልተወሰነለትም። አይሁድ፣ ሐማ እነርሱን ለማጥፋት ምቹ ነው ብሎ ያሰበውን (3፥7፡13 ይመ) የአዳር ወር ዐሥራ ሦስተኛ ቀን የጾም ቀን አድርገውታል፤ ይህንንም ጾም "የአስቴር ጾም" ብለው ይጠሩታል፤ ይህ ቀን ከፉሪም ክብረ በዓል አስቀድሞ የሚውል ቀን ነበር። ከአዳር ዐሥራ ሦስት እስከ ዐሥራ አምስት ያሉት፣ የእነዚህ ሦስት የድል መታሰቢያ የበዓል ቀናት መከበር በሥነ ጽሑፋዊ አቀራረቡ ሲታይ፣ አስቴር ንጉሡ ፊት ቀርባ ደጅ ከመጥናቷ አስቀድሞ (4፥16) ሦስት ቀን ከጾመችበት ጊዜ ጋር ሊገናዘብና ሊመዛዘን የሚችል ነው።

*10፥1-2፤* ጸሐፊው ስለ ግብር መጣል መጥቀሱ እርሱ ያገኘው ሌላ የታሪክ ምንጭ መኖሩን ያመለክታል፤ አንባቢም ተጨማሪ መረጃ እንዲያገኝና እንዲያረጋግጥ ይመራል (የ2፥23 ግብ ይመ)።

*10፥3፤* መርዶክዮስ ባገኘው የጠቅላይ ሚኒስትርነት ማዕረግ፣ ከስምንት ዓመት በላይ እንዳልቈየበት ይገመታል፤ ምክንያቱም በ465 ዓ.ቅ.ክ በእርሱ ቦታ ሌላ ሰው ተሹሞ እንደ ነበር የዓለም ታሪክ ይናገራል።

# መጽሐፈ ኢዮብ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ምንም እንኳ መጽሐፉ በአብዛኛው የያዘው የኢዮብንና የእርሱን አማካሪዎች ቃል ቢሆንም፣ የመጽሐፉ ጸሐፊ ግን ኢዮብ አይደለም:: ጸሐፊው (ኢዮብ ወይም የኢዮብ ወዳጆች ሳይሆኑ) እስራኤላውያን ለአምላካቸው መጠሪያ የሚጠቀሙበትን የቃል ኪዳን ስም ("ያህዌ" የሚለውን) በመጽሐፉ ውስጥ ብዙ ጊዜ ጠቅሶት በመገኘቱ፣ የዚህ መጽሐፍ ጸሐፊ እስራኤላዊ እንደ ሆነ እርግጠኞች መሆን እንችላለን:: በመጽሐፉ መግቢያ ላይ (ም 1-2)፣ እግዚአብሔር የኢዮብን ጥያቄ አስመልክቶ ገለጻ በሰጠበት ክፍልና (38፥1-42፥6) በመጽሐፉ መዝጊያ ላይ (42፥7-37) "እግዚአብሔር" (ያህዌ) የሚለው ቃል ብዙ ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን (በዕብራይስጡ ቅጅ ላይ 31 ጊዜ ተጠቅሶአል)፣ በተቀረው የመጽሐፉ ክፍል ግን ይህ ስም የተጠቀሰው (ም 3-37) አንድ ጊዜ ብቻ ነው (12፥9)::

ይህ ስሙ ያልተጠቀሰ ጸሐፊ ይህን መጽሐፍ አሁን ባለው ደረጃ በመንፈስ ቅዱስ መሪነት ጽፎ ያዘጋጀው፣ የሥነ ቃል ወይም የሥነ ጽሑፍ ምንጮችን መሠረት አድርጎ ሊሆን ይችላል:: በመግቢያው ላይ የሚገኘው ርእሰ ጉዳይ በቀጥታ በመለኮት የተገለጠ መሆን አለበት፤ ምክንያቱም ያንን ጉዳይ ከእግዚአብሔር በቀር ማንም ሊያውቀው አይችልም:: ጸሐፊው በርካታ ጥንታዊና እስራኤላዊ ያልሆኑ ዘይቤዎችን፣ ኢዮብና ወዳጆቹ በሚናገሩት ቋንቋ ውስጥ ጠብቆ ቢያቈይም፣ እንደ አንድ የጥበብ ጽሑፍ ጸሐፊ ግን የራሱን የአጻጻፍ ዘዬ ተከትሎ ጽፎአል:: የመጽሐፉ ሥነ ጽሑፋዊ ውቅርና የአገላለጹ ለዛ የጸሐፊውን ታላቅ የሥነ ጽሑፍ ችሎታ ያሳያል::

### መጽሐፉ የተጻፈበት ጊዜ

ይህ መጽሐፍ የተጻፈበትን ጊዜ አስመልክቶ ሁለት አስተያየቶች ተሰጥተዋል:- (1) መጽሐፉ የተጻፈው ኢዮብ በነበረበት ዘመንና ታሪካዊ ድርጊቱ በተፈጸመበት ዘመን ነው፤ (2) ታሪኩ ከተፈጸመ በኋላ፣ በመንፈስ ቅዱስ መሪነት መጽሐፉን አሁን ባለበት ደረጃ ባዘጋጀው ሰው ዘመን ነው:: ይህ ሁለተኛው ዘመን ከሰሎሞን ዘመነ መንግሥት አንሥቶ እስከ ምርኮ ባለው ዘመን መካከል ሊሆን ይችላል:: ምንም እንኳ ጸሐፊው እስራኤላዊ ቢሆንም፣ የእስራኤላውያንን ታሪክ በጽሑፉ ውስጥ አንድም ጊዜ አልጠቀሰም:: ጸሐፊው ይህን መጽሐፍ ሲያዘጋጅ ከእስራኤል ወገን ስላልነበረውና ጠቢብ ስለ ሆነው ሰው ስለ ኢዮብ (1፥1) የሥነ ጽሑፍና የሥነ ቃል ምንጮች ነበሩት፤ ኢዮብ የኖረው በሁለተኛው ሺህ ዓመት ዓ.ቅ.ክ. (2000-1000) ምናልባትም በዚሁ ሺህኛ ዓመት ማብቂያ ላይ ነው (የ19፥24 ማብ ይመ):: እንደ አይሁድ አባቶች ሁሉ፣ ኢዮብ ከ100 ዓመት በላይ ኖሮአል (42፥16):: የሀብቱ ብዛት የተለካው በቀንድና በጋማ ከብቶቹ ሲሆን (1፥3)፣ ቤተ ሰቡንም እንደ ካህን ሆኖ ያገለግል ነበር (1፥5)::

የሳባውያንና (1፥15) የከለዳውያን ነገዶች (1፥17) ወረራ እንዲሁም በ42፥11 ላይ "ብርና የወርቅ ቀለበት" የሚለው ሐረግ መጠቀሱ (ዘፍ 33፥19፤ ኢሱ 24፥32 ይመ)፤ ከሁለተኛው ሺህኛ ዓመት ጋር የሚስማማ ነው:: ከክርስቶስ ልደት በፊት በአንደኛው ወይም በሁለተኛው ምእተ ዓመት ላይ የተገኘውና 'ታርጉም' የተሰኘው ትርጒም (በአረማይስጥ ቋንቋ የተዘጋጀ የትርጒም ዐይነት ሲሆን ከዕዝራ፣ ከነህምያ፣ ከዳንኤልና ከኢዮብ መጻሕፍት ውስጥ ጥቂት ክፍሎች በዚህ ቋንቋ ተተርጒመዋል) የኢዮብ መጽሐፍ የተጻፈው በዚሁ ወቅት እንደ ሆነ ይናገራል፤ ሆኖም የዚህ አስተያየት ተቀባይነት አጠያያቂ ነው::

### መጽሐፉ የተጻፈበት ቋንቋና ትርጒሞች

በኢዮብ መጽሐፍ ውስጥ የምናገኛቸው በርካታ ያልተለመዱ ቃሎችና የአጻጻፍ ዘዬዎች፣ መጽሐፉን ከአንድ ቋንቋ ወደ ሌላ ቋንቋ ለመተርጐም አስቸጋሪ አድርገውታል:: ከዚህም የተነሣ በዚህ ዘመን የምናያቸው የመጽሐፉ ትርጒሞች ሰፊ ልዩነት ይታይባቸዋል:: ሌላው ቀርቶ የኢዮብን መጽሐፍ ወደ ግሪክ ቋንቋ የተረጐሙት ሰዎች (የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም) እንኳ ብዙ ጊዜ ግራ ተጋብተው ነበር:: የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም ከመደበኛው የዕብራይስጡ መጽሐፍ ጋር ሲነጻጸር በ400 ስንኞች አንሶ ይገኛል፤ ይህም የሰብዓ ሊቃናት ተርጓሚዎች ያልገባቸውን ስንኞች ሳይተረጒሟቸው ትተዋቸዋል ማለት ነው:: የቀድሞ የሱርስት፣ የአረማይስጥና የላቲን ተርጓሚዎችም ተመሳሳይ ችግር ገጥሞአቸው ነበር::

### የመጽሐፉ መሪ ሐሳብና መልእክት

የኢዮብ መጽሐፍ በፍትሐ አምላክ ጒዳይ ላይ ጥልቅ ትምህርት ይሰጣል (ፍትሐ አምላክ የእግዚአብሔር ቅን ፍርድ ከሰዎች መከራ ጋር ያለውን ተዛምዶ የሚመለከት ነው):: ሆኖም ስለ ፍትሐ አምላክ ያለው ግንዛቤና ለሚፈጥረውም ውዝግብ የተሰጠው መፍትሔ ፍጹም እስራኤላዊ ባሕርይ አለው:: በግሪክና በምዕራቡ ዓለም በፍትሐ አምላክ ጒዳይ ላይ የተነሣው ጥያቄ ከዚህ የሚከተለውን ይመስላል፤ "ክፉ በተንሰራፋበት ዓለም ውስጥ እግዚአብሔር ቅን ፈራጅ አምላክ ሊሆን የሚችለው

እንዴት ነው? ከሁሉም በላይ ንጹሓን መከራ የሚወርድባቸው ለምድን ነው?" ለእነዚህ ጥያቄዎች ሦስት መልሶች ተሰጥተዋል፤ (1)እግዚአብሔር ሁሉን ማድረግ የሚችል አምላክ አይደለም፤ (2) እግዚ አብሔር ቀና የሆነ ልቦና ያለው አምላክ አይደለም (በባሕርዩ ውስጥ ይብዛም ይነስ "ጨካኝነት" ይኖርበታል)፤ (3) ሰዎች ንጹሓን ሊሆኑ ይችላሉ:: ይሁን እንጂ በጥንት እስራኤላውያን አመለካከት መሠ ረት እግዚአብሔር ኀያል አምላክ፣ ፍጹም ቅን ፈራጅና ማንም ንጹሕ ሆኖ በእርሱ ፊት መቆም እንደ ማይችል የታመነ ነበር:: የኢዮብና የወዳጆቹ ሥነ መለኮት የተመሠረተው በእነዚህ ሦስት አመለካከ ቶች ላይ ነው:: ይህ ድምዳሜ የተገራው በቀላል አመክንዮ ነው:: ይኸውም ሰዎች መከራ የሚደርስባ ቸው በእግዚአብሔር ፊት በደለኞች ስለ ሆኑ ነው:: እንደ እውነቱ ከሆነ ይህን አባባል ከቶ መካድ አይቻልም፤ እንዲያውም አባባሉን ከአመንክንዮ አንጻር ከመረመርነው እውነት ሆኖ ይገኛል፤ ከሥነ መለኮት አንጻር ከፈተሽነው ትክክል ነው:: በመሆኑም በዚህ ዐይነት ሥነ መለኮት ላይ የተመሠረተ ፍትሐ አምላክ የሚያወዛግብና ግራ የሚያጋባ አይደለም፤ ምክንያቱም መፍትሔው ግልጽ ነው::

በሌላም በኩል መፍትሔው ግልጽ ነው ይባል እንጂ ከሰው ልጆች የሕይወት ተመክሮ ጋር ሲገ ናዘብ ብርቱ ውጥረት ምናልባትም ፍጭት ያስከትላል:: የኢዮብን ተመክሮ እንደ ምሳሌ የወሰድን እንደ ሆነ፣ ውጥረቱና ፍጭቱ ምን እንደ ሆነ በቀላሉ ማስተዋል ይቻላል:: ባካሄዳቸው ቅን የሆኑ ሰዎች አሉ፤ በምግባራቸው ጻድቅ የሆኑ ሰዎች አሉ፤ ኀጢአት የለሽ ባይሆኑም እንኳ፣ ራሳቸውን ከበደል ጠብቀው የሚኖሩ ሰዎች አሉ፤ ታዲያ፣ እንደዚህ ያሉ ሰዎች ብርቱ መከራ ሲደርስባቸው ይታያል:: እንደዚህ ላለው ውጥረትና ፍጭት ግልጽ መፍትሔ አለው ያልነው ሥነ መለኮት የሚያስገኘው ማጽናኛም ሆነ መመሪያ የለም:: ያስገኘልን ነገር ቢኖር ይበልጥ ምስጢር ማድረግ ብቻ ነው:: መከራና ችግር የደረሰባቸው ሰዎች የደረሰባቸውን ነገር እንዲያስወግድላቸው ወደ እግዚአብሔር ሲሄዱ እርሱ ራሱ የማይፈታ ምስጢር ይሆንባቸዋል:: ከም 3-37 በሚነበበው ንግግር ውስጥ የጻድቁ መከረኛ ነፍስ በአንድ በኩል እውነት አለን ከሚሉ ወገኖች የሚወረወርባት ፍላጻ መከራዋን ሲያባብስ ባት፣ በሌላ በኩል ደግሞ ከዚህ ታላቅ ምስጢር ጋር ትታገላለች:: ከዚህ በተጨማሪ ሁሉን መርምረን ደርሰንበታል የሚሉት ወዳጆቹ ቀኣስሉን እየወጉ ይበልጥ ያሠቃዩታል (5፥27 ማብ ይመ):: እዚህ ላይ እንግዲህ የፍትሐ አምላክ ምስጢር ጥልቅ እንደ ሆነ በጕልሕ ተንጸባርቆ እናያለን፤ እግዚአብሔር ቅን ፈራጅ አምላክ ከሆነ ጻድቃን መከራ የሚደርስባቸው ለምንድን ነው? የመለኮትስ ፍትሕ ወዴት ነው? ለእነዚህ ጥያቄዎች የተሰጠው "መልስ"ፍጹም እስራኤላዊ ወይም መጽሐፍ ቅዱሳዊ ነው:: በእግዚአብሔርና በሰው መካከል ያለው ግንኙነት ዝግ ግንኙነት ወይም ሌሎች ነገሮችን የሚያገል አይደለም:: በሁለቱ ግንኙነት ውስጥ ሌላ አካል እርሱም ታላቁ ባላጋራ ሲገባ ይታያል (ም 1-2 ይመ):: ይህ ባላጋራ እግዚ አብሔርን መቋቋምና መርታት ሲያቅተው የእግዚአብሔር ፍጥረት አውራ የሆነውንና በእግዚአብሔር አምሳል የተፈጠረውን ሰው ሊያሳምፅ ተነሣ:: ፈታኝ በመሆኑ ሰውን ከእግዚአብሔር ለመለየት ጕድጓድ ማስ (ዘፍ 3፤ ማቴ 4፥1 ይመ)፤ ከሳሽ በመሆኑ (ይህ ባላጋራ ከሚጠራበት ስም ውስጥ አንዱ "ሰይጣን" የሚል ነው፤ ትርጕሙም "ከሳሽ" ማለት ነው) እግዚአብሔርን ከሰው ለመለየት ላይ ታች ዋተተ (ዘካ 3፥1፤ ራእ 12፥9-10 ይመ):: ዓላማውም በእግዚአብሔርና በሰው መካከል ማብቂያ የሌ ለው ጠብና ጥላቻ እንዲቀሰቀስና ዳግም መታረቅ ወደማይቻሉበት ደረጃ እንዲደርሱ ነበር::

ስለ ኢዮብ በተነገረው ታሪክ ውስጥ ጸሓፊው ከፋውን ጠላት የሣለው በእግዚአብሔር ላይ የሚያሤርና በእግዚአብሔርና በሰው መካከል ያለውን መልካም ኅብረት ሰላም የሚነሣ ብርቱ ተፎካካሪ አድርጎ ነው:: እግዚአብሔር የኢዮብን ስም በከሳሹ ፊት ሲጠራና በምድር ሲኖር እንዴት ያለ ጻድቅ ሰው እንደ ሆነ ሲመሰክር፣ ሰይጣን በእግዚአብሔር የተወደደውን ሰው ለማጥፋትና እግዚአብሔር ሞኝ እንደ ሆነ ለማሳየት ሲጥር ይታያል:: በባሕርዩ ከሳሽ በመሆኑ ኢዮብን በእግዚአብሔር ፊት ይከሳል፤ ክሱም የኢዮብ ጽድቅ እኩይ ነው የሚል ነው:: እግዚአብሔር ደስ የተሰኘበት ጻድቅ ሰው አንድም መልካም ነገር የለበትም፤ ይህ ደግሞ የከፋ ኀጢአት ነው:: የኢዮብ ጽድቅ በግል ጥቅም ላይ የተመ ሠረተ ነው፤ ጽድቅ በእርሱ የተገኘው በሀብት ስለ ተባረከ ወይም እንጀራ ስለ ወጣለት ብቻ ነው:: በጽድቅና በበረከት መካከል ያለውን ትስስር በመለያየት ሰይጣን ኢዮብን እንዲፈትነው እግዚአብሔር ቢፈቅድለት፣ ጻድቁ ሰው ኀጢአተኛ መሆኑን በይፋ ያሳያል::

ይህ እንግዲህ ሰይጣን ይሳካልኛል ብሎ ያቀረበው ተንኰል ነበር:: እግዚአብሔር ደስ የሚሰኝበት የጻድቁ ሰው መንፈሳዊ ሕይወት ወይም ጽድቅ ከኀጢአት ሁሉ የከፋ ኀጢአት እንደ ሆነ ከታየ፣ በመካከላቸው ያለው ልዩነት መቼም ሊፈታ አይችልም ማለት ነው:: እንዲያውም እንዲህ ላሉ ሰዎች ቤዛነት የሚታሰብ አይሆንም፤ ምክንያቱም ከሰዎች ሁሉ እጅግ ጻድቅ የተባሉ ሰዎች እጅግ ርኩሳን ሆነው ተገኝተዋል:: ደግሞም እግዚአብሔር ፍጥረትን ለመቤዠት ያደረገው ሙከራ ከንቱ ሆኖአል:: እንግዲህ እግዚአብሔር ማድረግ ያለበት ሁሉንም ነገር በታላቅ ፍርዱ ዶጋ ዐመድ ማድረግ ብቻ ነው::

የክሱ ፋይል አንድ ጊዜ ከተከፈተ፣ ከዚህ በኋላ መዝጋት አይቻልም፤ ሌላው ቀርቶ የከሳሹን ድራሽ በማጥፋት ይህን እውን ማድረግ አይቻልም:: ስለዚህ እግዚአብሔር ከሳሹ (ዲያብሎስ)ኢዮብን እንዲያበጥረው (በተወሰነ ገደብ) ፈቀደለት፤ ይህንም ያደረገው የጻድቁ ኢዮብና የእግዚአብሔር ሥራ ይፋ እንዲሆንና ዲያብሎስ በሥራው እንዲያፍር ነው:: አሁን ኢዮብ በታላቅ ሥቃይ ውስጥ ወደቀ፤ በእግዚአብሔር ፊት ሞገስ እንዳገኘ የሚመሰክሩለትን ነገሮች ሁሉ ተገፈፈ፤ የእግዚአብሔርም አሠራር ግራ አጋባው፤ ታላቅ ምስጢርና እንቆቅልሽ ሆነበት:: ወዳጆቹ ሁሉ ይበልጥ የሚያደሙት እንጂ

የሚያሳርፋት አልሆኑም፤ ብቻውን በታላቅ ሐዘን ተቈራመደ:: ይሁን እንጂ በአካሄዱ ሁሉ ጻድቅ ሰው እንደ ሆነና እግዚአብሔርም አንድ ቀን በይፋ እንደሚመሰክርለት ያውቅ ነበር (13፥18፤ 14፥13-17፤ 16፥19፤ 19፥25-27 ይመ):: የተወለደበትን ቀን ቢረግምም (ም 3)፣ እግዚአብሔር ያለ በደሉ ፍጻውን ሲያሳየው በነገሩ እጅግ ቢያዝንም (9፥28-35)፣ እግዚአብሔርን ግን አልረገመም (ከማንም የምትቀር በው ሚስቱ ግን እግዚአብሔርን እንዲረግም መከራው ነበር፤ 2፥9 ይመ):: ኢዮብን እጅግ የሚጉዳው ግን እግዚአብሔር ትቶኛል የሚለው ሐሳብ ነው::

በመጨረሻ ግን ከሳሹ (ዲያብሎስ) እንዲያፍር ተደርጓል:: ሁሉን እናውቃለን የሚሉት የኢዮብ ወዳጆችም ኩም ተደርገዋል:: ራሱ ኢዮብም አፉን እንዲይዝ ተደርጓል:: እግዚአብሔር ግን ጻድቅ እንደ ሆነ ታየ:: እግዚአብሔር በተናገረ ጊዜ በቅድሚያ ያናገረው ኢዮብን ነው፤ እንዲህ ያደረገው መከራ በደረሰበት ጊዜ ከንቱ ንግግር በመናገሩ ሊያሳፍረውና ሁሉን ቻይ ከሆነው ከእግዚአብሔር ጋር በመከራከሩ ዝም ሊያሰኘው ነው (38፥1-42፥6 ይመ):: እግዚአብሔር የኢዮብ ሰማያዊ ወዳጅ እንደ መሆኑ መጠን፣ ኢዮብ ስለ ወዳጆቹ ያቀረበውን ምልጃ እግዚአብሔር ሰምቶአል (42፥8-10)፤ ኢዮብ ንም በዕጥፍ ባርኮታል (42፥10-17)::

እንግዲህ የዚህ መጽሐፍ ጸሓፊ እንደ አንድ መጋቢ የሚመክረን፣ ጻድቅ ሰው መከራ ቢደርስበት፣ ጽድቁ በእግዚአብሔር ዘንድ ዋጋ እንዳለውና እግዚአብሔርም ለዚያ ሰው ጽድቅ ትልቅ ቦታ እንደ ሚሰጥ ነው:: ታላቁ ከሳሽም ቢሆን የእግዚአብሔርን ሐሳብ ከንቱ ለማድረግ ከፈለገ፣ ጻድቁን ሰው ማሰናከል እንዳለበት ያውቃል:: በጻድቅ ሰው ላይ መከራና ሥቃይ የሚደርሰው፣ በሰማይ በታላቁ ባላጋራና (በዲያብሎስና) በእግዚአብሔር መካከል ብርቱ ትግል ስለሚደረግ ነው፤ ሆኖም በሁለት ኀያላን መካከል የሚደረግ ትግል አይደለም፤ ትግሉ ግን በእግዚአብሔር ቢጋር ውስጥ ስፍራ አለው:: በመሆኑም የጻድቁ ሰው መከራ ለዘመናት በቈየው ታላቁ መንፈሳዊ ትግል ውስጥ ትርጕምና ዋጋ አለው::

## የመጽሐፉ ሥነ ጽሑፋዊ ቅርጽና ውቅር

እንደ ሌሎች ጥንታውያን ሥነ ጽሑፎች ሁሉ፣ መጽሐፈ ኢዮብም በወጉ የተቀናጀ ሥነ ጽሑፋዊ ውቅር አለው፤ ይኸውም መግቢያ (ስድ ንባብ)፣ ሐተታና (ግጥም) መደምደሚያ (ስድ ንባብ) አለው:: እንዲህ ባለ ውቅር የተጻፈውም ባጋጣሚ ሳይሆን በሚገባ ታስቦበት ነው:: ኢዮብ የሚናገራቸው የሰቆቃና የወዮታ ቃሎች ናቸው (ም 3፤ እንዲሁም በንግግሩ ውስጥ የሚገኙትን አጫጭር ግጥሞች ይመ)፤ ሆኖም የኢዮብ የሰቆቃና የወዮታ ቃሎች በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ ብቻ የሚገኙና በመዝሙር መጽሐፍ ውስጥ ከምናገኛቸው (ከመዝ 88 በስተቀር) የሰቆቃ ቃሎች እጅግ የሚለዩ ናቸው:: አብዛኛው የመጽሐፉ ክፍል በሙግትና በክርክር መልክ የቀረበ ነው:: ምንም እንኳ ወዳጆቹ ሊያጽናኑት ቢመጡም፣ የመጡበትን ጒዳይ ዘንግተው በኢዮብ መከራ ላይ ሲከራከሩ ይታያል:: ይህ ክርክር በም 27 ላይ ጋብ ሲል፣ ኢዮብ ደግሞ ጻድቅ ሰው መሆኑን እግዚአብሔር እንዲመሰክርለት አቤቱታውን ያቀርባል (ም 29-31):: በጸሓፊው እይታ የኢዮብ ወዳጆች በሙግቱ የተሸነፉት ጥበብ የጐደላቸው ሰዎች ስለ ሆኑ ነው:: ስለዚህ እውነተኛ የሆነችውን ጥበብ ለማወደስ ሲል የመጽሐፉን ዐቢይ መልእክት ማዕከላዊ ስፍራ እንዲይዝ ያደረገው በሦስቱ እስጥ አገባ ሙግቶችና (ም 3-27) በሦስቱ አሐዳዊ ንግግሮች (ተዋሥኦ የሌለበት ወጥ ንግግር) መካከል ነው፤ እነዚህ አሐዳዊ ንግግሮች የኢዮብ (ም 29-31)፣ የኤሊሁና (ም 32-37) የእግዚአብሔር (38፥1-42፥6) ናቸው:: የኢዮብ አሐዳዊ ንግግር አማካሪዎቹ በእርሱ ላይ ያቀረቡት ክስ እውነተኛ ስላልሆነ እግዚአብሔር ቅን ፍርድ እንዲሰጠው ይጠይቃል:: የኤሊሁ አሐዳዊ ንግግር (ሰዎች መከራ የሚደርስባቸው በምን ምክንያት እንደ ሆነ ሰዎች የሚሰጡት ሌላው ምክንያት ነው) ኢዮብን እጅግ ከዘለፈ በኋላ፣ ስለ ቅጣት የተንሣውን መሪ ሐሳብ በመተው እግዚአብሔር ሰዎችን የሚቀጣው ወይም የሚያድነው ለምን እንደ ሆነ የራሱን ሐሳብ ይናገራል:: የእግዚአብሔር አሐዳዊ ንግግር ደግሞ የመለኮትን አስተያየት ይሰጣል፤ ኢዮብ በእግዚአብሔር አልተረገመም፤ ሆኖም በእርሱ ላይ ያ ሁሉ መከራ የደረሰው ለምን እንደ ሆነ አመክንዮአዊም ሆነ ሕጋዊ መልስ አልተሰጠም:: ይህ ለኢዮብ ምስጢር ነው፤ የዚህ መጽሐፍ አንባቢዎች ግን የኢዮብን መጨረሻ በመጽሐፉ መዝጊያ ላይ በግልጽ ለማየት ታድለዋል፤ ኢዮብ ከዚህ በፊት ከነበረው ሀብትና ንብረት ይበልጥ ዕጥፍ በረከት አግኝቶአል:: እንግዲህ የመጽሐፉ ሥነ ጽሑፋዊ ውቅርና ሥነ መለኮታዊ ፋይዳ ውብ በሆነ መንገድ በአንድነት ተጒንጒነዋል ማለት ይቻላል::

## አስተዋፅኦ

1. መግቢያ (ም 1-2)
   ሀ. የኢዮብ ደስታ (1፥1-5)
   ለ. የኢዮብ ፈተና (1፥6-2፥13)
      1. የሰይጣን የመጀመሪያው ክስ (1፥6-12)
      2. ኢዮብ ቤተ ሰቡንና ንብረቱን ባጣ ጊዜ ያሳየው እምነት (1፥13-22)
      3. የሰይጣን ሁለተኛው ክስ (2፥1-6)
      4. ኢዮብ መከራ በደረሰበት ጊዜ ያሳየው እምነት (2፥7-10)

5. የሦስቱ ወደጆቹ መምጣት (2፥11-13)
2. እሰጥ አገባና ሙግት (ም 3-27)
ሀ. የኢዮብ ሰቆቃ (ም 3)
ለ. የመጀምሪያው ዙር ንግግር (ም 4-14)
1. ኤልፋዝ (ም 4-5)
2. የኢዮብ መልስ (ም 6-7)
3. በልዳዶስ (ም 8)
4. የኢዮብ መልስ (ም 9-10)
5. ሶፋር (ም 11)
6. የኢዮብ መልስ (ም 12-14)
ሐ. ሁለተኛው ዙር ንግግር (ም 15-21)
1. ኤልፋዝ (ም 15)
2. የኢዮብ መልስ (ም 16-17)
3. በልዳዶስ (ም 18)
4. የኢዮብ መልስ (ም 19)
5. ሶፋር (ም 20)
6. የኢዮብ መልስ (ም 21)
መ. ሦስተኛው ዙር ንግግር (ም 22-26)
1. ኤልፋዝ (ም 22)
2. የኢዮብ መልስ (ም 23-24)
3. በልዳዶስ (ም 25)
4. የኢዮብ መልስ (ም 26)
ሠ. የኢዮብ የመዝጊያ ንግግር (ም 27)
3. በጣልቃ ገብነት ስለ ጥበብ የተነገረ ቃል (ም 28)
4. አሐዳዊ ንግግሮች (ተዋሥኦ የሌለባቸው ወጥ ንግግሮች) (29፥1-42፥6)
ሀ. ኢዮብ ቅን ሰው መሆኑን እግዚአብሔር እንዲመሰክርለት ያቀረበው አቤቱታ (ም 29-31)
1. የቀድሞ ክብሩና ሀብቱ (ም 29)
2. አሁን የደረሰበት ውርደትና ሥቃይ (ም 30)
3. በደል አልባ ስለ መሆኑ ያቀረበው አቤቱታና የመጨረሻው መሐላ (ም 31)
ለ. የኤሊሁ ንግግር (ም 32-37)
1. መግቢያ (32፥1-5)
2. ንግግሮቹ (32፥6-37፥24)
ሀ. የመጀመሪያው ንግግር (32፥6-33፥33)
ለ. ሁለተኛው ንግግር (ም 34)
ሐ. ሦስተኛው ንግግር (ም 35)
መ. አራተኛው ንግግር (ም 36-37)
ሐ. የእግዚአብሔር ማብራሪያ (38፥1-42፥6)
1. እግዚአብሔር የሰጠው የመጀመሪያ ማብራሪያ (38፥1-40፥2)
2. የኢዮብ መልስ (40፥3-5)
3. እግዚአብሔር የሰጠው ሁለተኛ ማብራሪያ (40፥6-41፥34)
4. የኢዮብ ንስሓ (42፥1-6)
5. መዝጊያ (42፥7-17)
ሀ. የእግዚአብሔር ቅን ፍርድ (42፥7-9)
ለ. ኢዮብ የቀድሞ ክብሩንና ሀብቱን ማግኘቱ (42፥10-17)

## መግቢያ

1 ዖፅ በሚባል አገር የሚኖር ኢዮብ የተባለ ሰው ነበረ፤ ይህ ሰው ነቀፋ የሌለበት፣ ቅን፣ እግዚአብሔርን የሚፈራና ከክፋት የራቀ ነበር። [2]እርሱም ሰባት ወንዶችና ሦስት ሴቶች ልጆች ነበሩት። [3]ሀብቱም ሰባት ሺህ በጎች፣ ሦስት ሺህ ግመሎች፣ አምስት መቶ ጥማድ በሬዎችና አምስት መቶ እንስት አህዮች ነበረ፤ እጅግ ብዙ ባሮችም ነበሩት፤ በምሥራቅ አገር ከሚኖሩትም ሰዎች ሁሉ ይልቅ እጅግ ታላቅ ሰው ነበረ።

[4]ወንዶች ልጆቹም ተራ በተራ በየቤታቸው ግብዣ ያደርጉ ነበር፤ ከእነርሱም ጋር እንዲበሉና እንዲጠጡ ሦስቱን እኅቶቻቸውን ይጋብዙ ነበር። [5]የግብዣው ጊዜ ካለፈ በኋላ ኢዮብ ልኮ ያስመጣቸውና፣ "ምናልባት ልጆቼ ኀጢአት ሠርተው እግዚአብሔርንም በልባቸው ረግመው ይሆናል" በማለት ጠዋት በማለዳ ስለ እያንዳንዳቸው የሚቃጠል መሥዋዕት በማቅረብ ያነጻቸው ነበር፤ ኢዮብ ይህን ዘወትር ያደርግ ነበር።

### የመጀመሪያው የኢዮብ ፈተና

[6]አንድ ቀን መላእክት[ሀ] በእግዚአብሔር ፊት ሊቆሙ በመጡ ጊዜ፣ ሰይጣንም[ለ] መጥቶ በመካከላቸው ቆመ። [7]እግዚአብሔርም ሰይጣንን፣ "ከወዴት መጣህ?" አለው።

ሰይጣንም፣ "በምድር ሁሉ ዞርሁ፤ ወዲያና ወዲህም ተመላለስሁባት" ብሎ ለእግዚአብሔር መለሰ።

[8]እግዚአብሔርም ሰይጣንን፣ "አገልጋዬን ኢዮብን ተመለከትኸውን? በምድር ላይ እንደ እርሱ ነቀፋ የሌለበት፣ ቅን፣ እግዚአብሔርን የሚፈራና ከክፋት የራቀ ሰው የለም" አለው።

[9]ሰይጣንም፣ ለእግዚአብሔር እንዲህ ሲል መለሰለት፣ "ኢዮብ እግዚአብሔርን የሚፈራው እንዲሁ ነውን? [10]በእርሱና በቤተ ሰቦቹ፣ ባለው ንብረትስ ሁሉ ዙሪያ ዐጥር ሠርተህለት የለምን? የበጎቹና የላሞቹ መንጋ ምድርን ሁሉ እስኪሞሉ ድረስ የእጁን ሥራ ባርከህለታል። [11]እስቲ፣ እጅህን ዘርግተህ ያለውን ሁሉ ንካበት፤ በእርግጥ ፊት ለፊት ይረግምሃል።"

[12]እግዚአብሔርም ሰይጣንን፣ "እነሆ፤ እርሱ ያለው ሁሉ በእጅህ ነው፤ እርሱን ራሱን ግን እንዳትነካው" አለው።

ከዚህ በኋላ ሰይጣን ከእግዚአብሔር ፊት ወጥቶ ሄደ።

1፥1 ቍ 8፤ዘፍ 6፥9፤ 10፥23፤22፥12፤ዘጸ 4፥6፤ኢዮ 2፥3፤23፥7፡10፤ መዝ 11፥7፤107፥42፤ ምሳ 21፥29፤ሕዝ 14፥14፡20፤ሚክ 7፥2፤1ተሰ 5፥22፤ያዕ 5፥11
1፥2 ቍ 13፡18፤ሩት 4፥15፤ኢዮ 42፥13፤ መዝ 127፥3፤144፥12
1፥3 ቍ 8፤ዘፍ 12፥16፤13፥2፤25፥6፤ኢዮ 29፥25፤42፥10፤መዝ 103፥10
1፥4 ቍ 13፡18
1፥5 ዘፍ 8፥20፤1ነገ 21፥10፡13፤ነህ 12፥30፤ ኢዮ 8፥4፤መዝ 10፥3፤ 74፥10
1፥6 ዘፍ 6፥2፤2ሳሙ 24፥1፤1ነገ 22፥19፤ 2ዜና 18፥21፤ኢዮ 2፥1፤መዝ 109፥6፤ሉቃ 22፥31
1፥7 ዘፍ 3፥1፤1ጴጥ 5፥8
1፥8 ቍ 1፤ዘፀ 20፥20፤ኢሳ 1፥7፤መዝ 25፥12፤112፥1፤128፥4
1፥9 1ጢሞ 6፥5
1፥10 ቍ 3፡12፤ 1ሳሙ 25፥16፤ኢዮ 2፥4፤8፥7፤29፥6፤42፥12፤ 17፤መዝ 34፥7
1፥11 ዘሌ 24፥11፤ ኢዮ 2፥5፤19፥21፤ኢሳ 3፥8፤65፥3፤ ሉቃ 22፥31፤ራዕ 12፥9-10
1፥12 ቍ 10፤ኢዮ 2፥6፤1ቆሮ 10፥13

[ሀ] 6 በዕብራይስጡ የእግዚአብሔር ልጆች ይላል

[ለ] 6 ሰይጣን ማለት ከሳሽ ማለት ነው

1፥1 *ዖፅ በሚባል አገር፤* ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ የሚገኝ (ቍ 3 ይመ)፣ በደቡብ ኤዶምን (ዘፍ 36፥28፤ ሰቆ 4፥21 ይመ)፣ በሰሜን ደግሞ የአራምን ምድር የሚያካትት (ዘፍ 10፥23፤ 22፥21 ይመ) ሰፊ ግዛት ነበር። *ነቀፋ የሌለበት፣ ቅን፤* በመንፈሳዊና በግብረገባዊ ሕይወቱ እንከን የማይገኝበት ማለት ነው፤ ይህ ማለት ግን ኢዮብ ኀጢአት የለበትም ማለት አይደለም። በኋላም ኢዮብ ጻድቅ ሰው መሆኑን ቢገልጽም፣ ኀጢአተኛ መሆኑን አልደበቀም? (6፥24፤ 7፥21 ይመ)። እግዚአብሔርን *የሚፈራ፤ 28፥28፤* ምሳ 3፥7 እንዲሁም የዘፍ 20፥11 ማብ ይመ።

1፥2 *ሰባት ወንዶችና፤* ፍጹምነትን የሚያመለክት ቍጥር ነው (የሩት 4፥15 ማብ ይመ)።

1፥3 *ሰባት ሺህ በጎች፤* የ42፥12 ማብ ይመ። የኢዮብ ሀብቱ መሬት ሳይሆን የቤት እንስሳት ነበሩ (ዘፍ 12፥16፤ 13፥2፤ 26፥14 ይመ)። *አህዮች፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ እንስት አህዮችን ያመለክታል፤ ወላድ አህዮችም ከፍተኛ ዋጋ ነበራቸው። *በምሥራቅ አገር ከሚኖሩትም ሰዎች፤* ይህ ሐረግ በዕብራይስጡ የምስራቅ ሰዎች ተብሎ ተተርጕሞአል (ዘፍ 29፥1፤ መሳ 6፥3 እና ማብ ይመ)።

1፥5 *የግብዣው ጊዜ፤* ለየት ያለ ሥርዐት የሚጠይቁ ግብዣዎች ሳምንቱን ሙሉ የሚካሄዱበት ጊዜ ነበር (ዘፍ 29፥27፤ መሳ 14፥12 ይመ)። *መሥዋዕት በማቅረብ ያነጻቸው ነበር፤* የሙሴ የመንጻት ሕግ ከመውጣቱ በፊት የቤተ ሰብ ኀላፊ የሆነው ሰው እንደ ካህን ያገለግል ነበር (ዘፍ 15፥9-10 ይመ)። *ያነጻቸው ነበር፤* ለሚያቀርብላቸው መሥዋዕት ይዘጋጁ ዘንድ በሥርዐቱ መሠረት እንዲነጹ ያደርግ ነበር (በዘፀ 19፥10፡14 ላይ ለዚህ ሐረግ የተሰጠው የዕብራይስጥ ቃል "ይቀድሳቸው" ነበር የሚል ነው)።

1፥6 *መላእክት—ሊቆሙ በመጡ ጊዜ፤* ለዚህ ቍጥር እንዲሁም ለ2፥1 እና 38፥7 በአግራፉ የቀረበውን ማብ ይመ። በእግዚአብሔር ፊት ቆሙ (1ነገ 22፥19፤ መዝ 89፥5-7፤ ኤር 23፥18፡22)። *ሰይጣንም፤* በቁሙ "ከሳሽ" ማለት ነው (በአግራፉ የቀረበውን ማብ እንዲሁም ራእ 12፥10 ይመ)። በዕብራይስጡ የኢዮብ መጽሐፍ ይህ ቃል ምን ጊዜም የተወሰነ መስተአምርን ተከትሎ ይገባል፤ ነገር ግን በዕብራይስጡ 1ዜና 21፥1 ላይ የተወሰነ መስተአምር የለውም፤ ምክንያቱም "ሰይጣን" የሚለው ቃል በዚያን ጊዜ የተጸውዖ ስም ሆኖአልና፤

1፥7 *እግዚአብሔርም፤* እስራኤላውያን እግዚአብሔርን የሚጠሩበት የቃል ኪዳን ስም ነው። *ሰይጣንን፤* ከዚህ ምንባብ የምንረዳው ሰይጣን አካላዊ ሕልውና ያለው ፍጡር እንጂ ለክፋት የሚንሥጣ ኀይል ብቻ አይደለም፤ ስለዚህም 1) አእምሮ ስላለው ከእግዚአብሔር ጋር ተነጋገረ፤ 2) ስሜት ስላለው ኢዮብን ጠላው (ቍ 9-11)፤ 3) ፈቃድ ስላለው ኢዮብን ለማጥፋት ፈለገ (1፥11፤ 2፥4-5፡7)፤ የክፋት ሥራው ግን በልዑል እግዚአብሔር ቍጥጥር ሥር ነበር (1፥12፤ 2፥6)። በመጽሐፍ ቅዱስ ሰይጣን አካላዊ ሕልውና ያለውና መንፈሳዊ ፍጡር ነው። ሰይጣን ማለት "ባላጋራ" ማለት ነው፤ ይህም የእግዚአብሔርንና የማንነቱ፣ የእግዚአብሔር ሕዝብና የእግዚአብሔር ዕቅድ ተቃዋሚ መሆኑን የሚገልጽ ነው።

1፥8 *ኢዮብን ተመለከትኸውን?* ጌታ ራሱ ወደ ፈተና የሚያመራውን ጥያቄ በማቅረብ ነገሩን አነሣ፤ ኢዮብ በምንም ዐይነት በጠላት ሊከሰስ የማይችል ጻድቅ ሰው መሆኑንም እግዚአብሔር ተናገረ። *አገልጋዬ፤* 42፥7-8 እና በአግራፉ የቀረበውን ትርጕም ማብ ይመ። ከእግዚአብሔር ጋር የተለየ ግንኙነት ያለውንና በአገልግሎቱም ታማኝ የሆነውን ሰው ያመለክታል (ለምሳሌ ሙሴን በዘኍ 12፥7፤ ዳዊትን በ2ሳሙ 7፥5 እንዲሁም በኢሳ 42፥1፤ 52፥13፤ 53፥11 ይመ)።

*1፥9* እግዚአብሔር የመረጠውን፣ ሰይጣን በድፍረት ይከሰዋል፤ እግዚአብሔር የተደሰተበትን የኢዮብን ጽድቅ ሰይጣን በግል ጥቅም ፍላጎት ላይ የተመሠረተ አድርጎ አቀረበው፤ ይህም በመጽሐፈ ኢዮብ ውስጥ ሰይጣን እግዚአብሔርን የእርሱን ታማኝ አገልጋይ ለመዋጋት የተጠቀመበት ዋና ነጥብ ነው።

1፥10 ዐጥር፤ በመከላከያ በምሳሌነት የቀረበ ነው (ኢሳ 5፥5 ይመ ከኢዮ 3፥23 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥11 *እጅህን ዘርግተህ.. ንካበት፤* 4፥5 ይመ።

*1፥12፤* ሰይጣን ኢዮብን እንዲያሠቃየው ሥልጣን ተሰጥቶታል (ቍ 5)፤ ነገር ግን ገደብ ተደርጎበታል (ቍ 12)። ሰይጣን በሰው ላይም ሆነ (ቍ 15፡17) በተፈጥሮ ላይ (16፡19) በሚያደርሰው ክፋት ሁሉ በኀያሉ በእግዚአብሔር ሥልጣን ሥር ነው (1ዜና 21፥15፤ ከ2ሳሙ 24፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም 1ሳሙ 16፥14፤ 2ሳሙ 24፥16፤ 1ቆሮ 5፥5፤ 2ቆሮ 12፥7፤ ዕብ 2፥14 ይመ)፤ ይህን እንጂ ውጊያው በቀላሉ የሚታይ አይደለም። ኢዮብ በእርሱ ፊት እግዚአብሔርን ይከሳልን? ኢዮብ ካልከሰሰ ደግሞ ሰይጣን ሐሰተኛ መሆኑ ይረጋገጣል፤ እግዚአብሔር በኢዮብ ደስ መሰኘቱም በከንቱ እንዳልሆነ ይታወቃል።

[13]አንድ ቀን የኢዮብ ወንዶችና ሴቶች ልጆች በታላቅ ወንድማቸው ቤት ተሰብስ በው ይበሉና የወይን ጠጅ ይጠጡ ነበር፤ [14]መልእክተኛም ወደ ኢዮብ መጥቶ እንዲህ አለው፤ "በሬዎች እያረሱ፣ አህዮችም በአጠገ ባቸው እየጋጡ ሳሉ፣ [15]ሳባውያን ጥቃት አድርሰውባቸው ይዘዋቸው ሄዱ፤ አገልጋዮ ቹንም በሰይፍ ገደሉ:: እኔም ብቻዬን አመ ለጥሁ፤ ልነግርህም መጣሁ::"

[16]እርሱም እየተናገረ ሳለ፣ ሌላ መልእ ክተኛ መጥቶ፣ "የእግዚአብሔር እሳት ከሰማይ ወረደች፤ በጎችንና አገልጋዮችንም በላች፤ እኔም ብቻዬን አመለጥሁ፤ ልነግርህም መጣሁ" አለው::

[17]እርሱም እየተናገረ ሳለ፣ ሌላ መልእ ክተኛ መጥቶ፣ "ከለዳውያን በሦስት ቡድን መጥተው ጥቃት አደረሱ፤ ግመሎችህንም ይዘው ሄዱ፤ አገልጋዮቹን በሰይፍ ገደሉ፤ እኔም ብቻዬን አመለጥሁ፤ ልነግርህም መጣሁ" አለው::

[18]እርሱም እየተናገረ ሳለ፣ ሌላ መልእ ክተኛ መጥቶ እንዲህ አለው፤ "ወንዶችና ሴቶች ልጆችህ በታላቅ ወንድማቸው ቤት ተሰብስበው እየበሉና እየጠጡ ሳሉ፣ [19]እነሆ፤ ታላቅ ዐውሎ ነፋስ ከምድረ በዳ መጣ፤ የቤቱንም አራት ማእዘናት መታ፤ እርሱም በልጆቹ ላይ ወድቆ ገደላቸው:: እኔም ብቻ ዬን አመለጥሁ፤ ልነግርህም መጣሁ::" [20]ኢዮ ብም ተነሣ፤ ልብሱን ቀደደ፤ ራሱን ተላጨ፤ በምድርም ላይ ተደፍቶ ሰገደ፤ [21]እንዲህም አለ፤

"ዕራቍቴን ከእናቴ ማሕፀን ወጣሁ፤
ዕራቍቴንም እሄዳለሁ::ሐ
እግዚአብሔር ሰጠ፤ እግዚአብሔር ነሣ፤
የእግዚአብሔር ስም ቡሩክ ይሁን::"

1፥13 ቍ2፡4
1፥14 ዘፍ36፥24
1፥15 ዘፍ10፥7፤ ኢዮ9፥24
1፥16 ዘፍ18፥17፤ ዘሌ10፥2፤ዘኍ11፥1-3፤1ነገ18፥38፤2ነገ1፥12፤ኢዮ20፥26
1፥17 ዘፍ11፥28፤ ኢዮ9፥24
1፥18 ቍ2፡4
1፥19 ኢዮ16፥7፤ 19፥13-15፤መዝ11፥6፤ኢሳ5፥28፤21፥1፤ ኤር4፥11፤13፥24፤ 18፥17፤ሕዝ17፥10፤ 24፥26፤ሆሴ13፥15፤ ማቴ7፥25
1፥20 ዘፍ37፥29፤ ኢሳ3፥24፤15፥2፤22፥12፤ኤር7፥29፤16፥6፤ ሕዝ27፥31፤29፥18፤ ሚክ1፥16፤ማር14፥63፤1ጴጥ5፥6
1፥21 መክ5፥15፤ሩት1፥21፤1ሳሙ2፥7፤ኢዮ2፥10፤መክ7፥14፤5፥15፤ ኤር44፥2፤ኤፌ5፥20፤1ተሰ5፥18፤1ጢሞ6፥7፤ያዕ5፥11
1፥22 ኢዮ2፥10፤ መዝ39፥1፤ምሳ10፥19፤13፥3፤ኢሳ53፥7፤ ሮሜ9፥20
2፥1 ዘፍ6፥21 ኢዮ1፥6
2፥2 ዘፍ3፥1
2፥3 ዘፀ20፥20፤ኢዮ1፥1፤16፥29፤9፥17፤13፥18፤27፥6፤31፥6፤32፥1፤40፥8፤መዝ44፥17
2፥4 ኢዮ1፥10
2፥5 ዘፀ20፥7፤ኢዮ1፥11፤16፥8፤19፥20፤33፥21፤መዝ102፥5፤ ሰቈ4፥8
2፥6 ኢዮ 1፥12፤ 2ቆሮ12፥7

[22]በዚህ ሁሉ፣ ኢዮብ አልበደለም፤ በእግዚአ ብሔርም ላይ ክፉ አልተናገረም::

## ሁለተኛው የኢዮብ ፈተና

**2** በሌላ ቀን ደግሞ፤ መላእክት[ሠ] በእግዚ አብሔር ፊት ለመቆም መጡ:: ሰይ ጣንም ከእነርሱ ጋር በእግዚአብሔር ፊት ሊቆም መጣ:: [2]እግዚአብሔር ሰይጣንን፣ "ከወዴት መጣህ?" አለው::

ሰይጣንም፣ "በምድር ሁሉ ዞርሁ፤ ወዲያና ወዲህም ተመላለስሁባት" ብሎ ለእግዚአ ብሔር መለሰ::

[3]እግዚአብሔርም ሰይጣንን፣ "አገልጋዬን ኢዮብን ተመለከትኸውን? በምድር ላይ እንደ እርሱ ነቀፋ የሌለበት፣ ቅን፣ እግዚአ ብሔርን የሚፈራና ከክፉት የራቀ ሰው የለም፤ ያለ ምክንያት እንዳጠፋው ብትወተውተኝም፣ ይኸው ፍጹምነቱን እንደ ጠበቀ ነው" አለው::

[4]ሰይጣንም እንዲህ ሲል መለሰ፤ " 'ቍርበት ስለ ቍርበት ነው' እንዲሉ ሰው ለሕ ይወቱ ሲል ያለውን ሁሉ ይሰጣል፤ [5]እስቲ እጅህን ዘርግተህ ዐጥንቱንና ሥጋውን ዳስ፤ በእርግጥ ፊት ለፊት ይሰድብሃል::"

[6]እግዚአብሔርም ሰይጣንን፣ "እነሆ፤ እርሱ በእጅህ ነው፤ ሕይወቱን ግን እንዳትነካ" አለው::

[7]ከዚህ በኋላ ሰይጣን ከእግዚአብሔር ፊት ወጥቶ ሄደ፤ ኢዮብንም ከእግር ጥፍሩ እስከ ራስ ጠጕሩ በክፉ ቍስል መታው:: [8]ኢዮ ብም ገላውን ለማከክ ገል ወሰደ፤ በዐመ ድም ላይ ተቀመጠ::

2፥7 ዘዳ28፥35፤ኢዮ16፥16

ሐ21 ወይም ወደዚያ እመለሳለሁ
ሠ1 የዕብራይስጡ የእግዚአብሔር ልጆች ይላል

1፥15 *ሳባውያን፤* ትውልዶቻቸው በቅመማ ቅመም፣ በወርቅና በከበሩ ድንጋዮች የበለጸጉ የደቡብ ዐረቢያ ነዋሪዎች ሳይሆኑ አይቀሩም (የንግሥተ ሳባን ታሪክ በ1ነገ 10፥1-13 ይመ እንዲሁም መዝ 72፥10፡15፤ ኢሳ 60፥6፤ ኤር 6፥20፤ ሕዝ 27፥22፤ ኢል 13፥8 ይመ):: በኢዮ 6፥19 ላይ ሳባውያን፣ ተዘዋዋሪ ነጋዴዎች ተብለዋል፤ ይህም ከኢየሩሳሌም አምስት መቶ ስድሳ ኪሎ ሜትር ርቃ ከምትገኘው ከቴማ አገር የመጡ ሰዎች እንደሆኑ ይነገራል::

1፥16 *የእግዚአብሔር እሳት፤* መብረቅ (ዘኍ 11፥1፤ 1ነገ 18፥38፤ 2ነገ 1፥12 ይመ)::

1፥17 *ከለዳውያን፤* እስከ አንድ ሺህ ዓ.ቅ.ክ አካባቢ (በደቡብ መስጴጦምያ በሰፈሩ ጊዜ) በድዊን ይባሉ የነበሩ ሕዝ ቦች ናቸው:: በኋላም በናቡከደነፆር ዘመነ መንግሥት እነዚህ ሕዝ ቦች ዐይነተኛ ሰፍራ ነበራቸው::

1፥19 *ታላቅ ዐውሎ ነፋስ፤* ኀይለኛና ብርቱ ነፋስ ነው::

1፥20 *ኢዮብም ተነሣ፤* ልጆቹ እስኪገደሉ ድረስ በጸጥታ ቈየ፤ *ልብሱን ቀደደ፣ ራሱን ተላጨ፤* ከማዘኑ የተነሣ ነበር (የዘፍ 37፥34፤ የኢሳ 15፥2 ማብ ይመ)::

1፥21 *እሄዳለሁ፤* ዘፍ 2፥7፤ 3፥19 እና ማብ ይመ:: *እግዚ አብሔር ሰጠ፤ እግዚአብሔር ነሣ፤* የኢዮብ እምነት የልዑል እግዚአብሔር አሠራር እንዴት እንደ ሆነ አሳየው፤ ይህም ከባድ መከራ በደረሰበት ጊዜ መጽናኛ ሆኖታል::

*2፥1-3፤* ከመጨረሻው ዐረፍተ ነገር በቀር ይህ ክፍል በ1፥6-8 ላይ ከተገለጸው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይ ነው፤ ኢዮብን፣ አታላይ የሆነ ዐላማ አለው ብሎ የከሰሰው ፍጡር በዚህ ጊዜ እርሱ ራሱ አታላይ የሆነ ዐላማ እንዳለው ይፋ ሆነ:: ይህ አታላ ይና ድብቅ ዐላማም በኢዮብ በኩል ሆኖ እግዚአብሔርን ለማሳ ጣት ነበር::

2፥3 *ብትወተውተኝም፤* የሚሆነው ነገር ሁሉ ከመለኮ ታዊ ዕቅድ ጋር መጣጣሙን መገንዘብ ቢያስቸግርም እንኳ (38፥2 ይመ) ከፈቃዱ ውጭ እንዲሠራ በእግዚአብሔር ላይ ተጽእኖ ሊያደ ርግበት አይችልም::

2፥4 *ቍርበት ስለ ቍርበት፤* ምሳሌያዊ አነጋገር መሆኑ ግልጽ ነው፤ የአንዱን እንስሳ ቈዳ ተመሳሳይ ዋጋ ካለው ከሌላ እንስሳ ቈዳ ጋር በመለዋወጥ ገበያ ላይ የተመሠረተን አባባል ሊያመለክት ይችላል::

2፥5 *ዐጥንቱንና ሥጋውን ዳስ፤* 1፥11-12 ይመ:: ከዘፍ 2፥23፤ ከሉቃ 24፥39 ጋር ያነጻጽሩ::

2፥6 *ሕይወቱን ግን እንዳትነካ፤* አሁን እንኳ ሰይጣን የእ ግዚአብሔር ገደብ እንደተጣለበት ነው:: ኢዮብ ቢሞት ኖሮ የእ ግዚአብሔርም ሆነ የራሱ ትክክለኛነት በግልጽ አይታወቅም ነበር::

*2፥7፤* የኢዮብ ሕመም ምን እንደ ሆነ በትክክል ማወቅ አይቻልም፤ ሆኖም የሕመሙ ምልክት፣ ሥቃይ ያለበት መግል የያዘ እባጭ በሰውነቱ ሁሉ ግልብጥ ብሎ መታየቱ (7፥5)፣ ቅዠት (7፥14)፣ የቈዳው ቍስል፣ መገልፈፍና መጥቈር (30፥28፡30)፣ መልኩ፣ አስከፊ፤ አስፈሪና ዘግናኝ ሆኖ መታየቱ (2፥12፤ 19፥19)፣ የትንፋሹ መከርፋት (19፥17)፣ መክሳት፣ መመንመን (17፥7፤ 19፥20)፣ ትኩሳቱ (30፥30)፣ ቀንና ሌሊት ዕረፍት የሚነሣው ሥቃዩ (30፥17) ናቸው:: *በክፉ ቍስል፤* በዘዳ 9፥9፤ በዘሌ 13፥18፤ በ2ነገ 20፥7 ላይ በዕብራይስጡ ይህ ሐረግ፣ "ዕባጭ" ተብሎ ተተርጕሞአል::

2፥8 *በዐመድም፤* የሐዘን ምልክት ነው (42፥6፤ አስ 4፥3

[9]ሚስቱም፣ "አሁንም ታማኝነትህን አል ተውህምን? ይልቁን እግዚአብሔርን ርገምና ሙት!" አለችው

[10]እርሱም፣ "አነጋገርሽ እንደማታስተውል[ሠ] ሴት ነው፤ መልካሙን ነገር ከእግዚአብሔር ዘንድ ተቀበልን፣ ክፉውንስ አንቀበልምን? አላት።

በዚህ ሁሉ፣ ኢዮብ በንግግሩ አልበደለም።

## ሦስቱ የኢዮብ ወዳጆች

[11]ሦስቱ የኢዮብ ወዳጆች ቴማናዊው ኤል ፋዝ፣ ሹሐዊው በልዳዶስ፣ ናዕማታዊውም ሶፋር በኢዮብ ላይ የደረሰውን መከራ ሁሉ በሰሙ ጊዜ፣ ሄደው ሊያስተዛዝኑትና ሊያ ጽናኑት በመስማማት ከየመኖሪያቸው በአን ድነት መጡ። [12]እነርሱም ከሩቅ ሆነው ሲመ ለከቱት እርሱ መሆኑን ሊለዩ አልቻሉም፤ በዚህ ጊዜ ድምፃቸውን ከፍ አድርገው አለ ቀሱ፤ ልብሳቸውንም ቀደው በራሳቸው ላይ ትቢያ ነሰነሱ። [13]ሰባት ቀንና ሰባት ሌሊት ከእርሱ ጋር መሬት ላይ ተቀመጡ፤ ሥቃዩ ታላቅ መሆኑንም ስለ ተረዱ፣ አንዳች ቃል የተናገረው አልነበረም።

## ኢዮብ ይናገራል

**3** ከዚህ በኋላ፣ ኢዮብ አፉን ከፍቶ የተወ ለደበትን ቀን ረገመ፤ [2]እንዲህም አለ፤

[3]"የተወለድሁበት ቀን ይጥፋ፣
'ወንድ ልጅ ተፀነሰ' የተባለበት ሌሊት።
[4]ያ ቀን ጨለማ ይሁን፤
እግዚአብሔር ከላይ አይመልከተው፤
ብርሃንም አይብራበት።
[5]ጨለማና የሞት ጥላ[ረ] ይውረሱት፤
ደመናም በላዩ ላይ ይረፍ፤
ብርሃኑን ጽልመት ይዋጠው።
[6]ያ ሌሊት በድቅድቅ ጨለማ ይያዝ፤
ከዓመቱ ቀናት ጋር አይቈጠር፤
ከወራቱ በአንዱም ውስጥ አይግባ።
[7]ያ ሌሊት መካን ይሁን፤
እልልታም አይሰማበት።
[8]ሌዋታንን ለማነሣሣት የተዘጋጁ፣
ቀንንም[ሰ] የሚረግሙ ያን ቀን
ይርገሙት።
[9]አጥቢያ ኮከቦቹ ይጨልሙ፤
ብርሃንን እየጠበቀ ይጣ፣
የንጋት ጮራ ሲፈነጥቅ አይይ።
[10]መከራን ከዐይኔ ይሰውር ዘንድ፣
የእናቴን ማሕፀን ደጅ በላዬ
አልዘጋምና።
[11]"ምነው ገና ስወለድ በጠፋሁ!
ምነው ከማሕፀን ስወጣ በሞትሁ!
[12]የሚቀበሉኝ ጕልበቶች፤
የሚያጠቡኝ ጡቶች ለምን ተገኙ?
[13]ይህን ጊዜ በሰላም በተኛሁ፣
አንቀላፍቼም ባረፍሁ ነበር፤
[14]አሁን ፈርሶ የሚታየውን ስፍራ ለራሳቸው
ካሠሩት፣
ከምድር ነገሥታትና ከአማካሪዎች ጋር፣
[15]ቤታቸውን በብር ከሞሉ፣
ወርቅም ከነበራቸው ገዦች ጋር
ባረፍሁ ነበር።

2፥8 ዘፍ18፥27፤ሶስ 4፥3፤ኢዮ16፥15፤19፥9፤30፥19፤42፥6፤መዝ 7፥5፤ኢሳ58፥5፤61፥3፤ኤር6፥26፤ሰቆ3፥29፤ሕዝ26፥16፤ዮና 3፥5-8፤ማቴ11፥21
2፥9 ዘፀ20፥7፤2ነገ 6፥33፤ኢዮ6፥29፤13፥15፤27፥5፤33፥9፤35፥2፤1ተሰ5፥8
2፥10 ኢዮ1፥21፡ 22፤6፥24፤መክ2፥24፤ሰቆ3፥38፤ያዕ1፥12፤5፥11
2፥11 ዘፍ25፥2፤ 36፥11፤37፥35፤ኢዮ 6፥10፤11፥1፤20፥1፤ዮሐ11፥19
2፥12 ዘፍ37፥29፤ ኢሱ7፥6፤2ሳሙ1፥2፤ 15፥23፤ኢዮ17፥7፤ኢሳ52፥14፤ማር14፥63
2፥13 ዘፍ50፥10፤ ምሳ17፥28፤ኢሳ3፥26፤ 23፥2፤47፥1፡5፤ ኤር48፥18፤ሰቆ2፥10፤ ሕዝ26፥16፤ዮና3፥6፤ሐጌ2፥22
3፥1 ኤር15፥10፤ 20፥14
3፥3 ኦሪ11፡16፤ኢዮ 10፥18-19፤መክ4፥2፤ 6፥3፤ኤር20፥14-18፤ ማቴ26፥24
3፥5 ኢዮ10፥21፡ 22፤ 34፥22፤38፥17፤ መዝ23፥4፤44፥19፤88፥12፤ኤር2፥6፤13፥16
3፥6 ኢዮ23፥17፤ 30፥26
3፥7 መዝ20፥5፤33፥3፤65፥13፤ኢሳ26፥19፤ ኤር51፥48
3፥8 ዘፍ1፥21፤ኢዮ 10፥18፤41፥1፡8፡10፡ 25፤መዝ74፥14፤104፥26፤ኤር20፥14
3፥9 ኢዮ41፥18፤ ዕን3፥4 3፥11 ኦሪ3 3፥12 ዘፍ48፥12፤ኢሳ66፥12 3፥13 ኦሪ7፤ኢዮ7፥8-10፡21፤10፥22፤13፥19፤14፥10-12፤17፥13፤19፥27፤21፥13፡23፤27፥19፤30፥23፤መዝ139፥11፤ኢሳ8፥22 3፥14 ኢዮ9፥24፤12፥17፤15፥28፤ኢሳ14፥9፤ኤር51፥37፤ሕዝ32፥28-32፤ናሆ3፥7 3፥15 ኢዮ12፥21፤ 15፥29፤20፥10፤27፥17፤መዝ49፥16-17፤ምሳ 13፥22፤28፥8፤መክ2፥26፤ኢሳ2፥7፤ 45፥1፤ሶፎ1፥11

[ሠ]10 *እንደማታስተውል* ተብሎ የተተረጐመው የዕብራይስጥ ቃል ገብረ ገባዊ ሕጸጽን ያመለክታል
[ረ]5 *ወይም ከባድ ጥላ*
[ሰ]8 *ወይም ባሕርን*

ይመ፤ ከዮና 3፥6 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥9 ***እግዚአብሔርን ርገምና፤*** በዚህ ስፍራና በ1፥5 ላይ ለተጠቀሰው ለዚህ ሐረግ የገባው የዕብራይስጥ ቃል ዘይቤያዊ አገላለጽ አለው (ቃሉ በቁሙ፣ "እግዚአብሔርን ባርክ" አለው)። ሰይጣን አዳምን ለመፈተን ሔዋንን መሣሪያ እንዳደረጋት ሁሉ ኢዮብንም ለመፈተን ሚስቱን መሣሪያ አድርጎ ተጠቅሞባታል። ***ሙት፤*** ሞቱን ከመጠባበቅ በቀር ለኢዮብ የተረፈው ነገር ባለመኖሩ ሚስቱ፣ ባሏ እግዚአብሔርን በመስደብ ሞቱን እንዲ ጋብዝ ገፋፋችው (ዘሌ 24፥10-16)።

2፥10 ***መልካሙን ነገር ከእግዚአብሔር ዘንድ ተቀበልን፤ ክፉውንስ አንቀበልምን?*** የመጽሐፉ መሪ ሐሳብ ነው፤ በክርስ ቲያን ላይ መከራና ሥቃይ የሚደርሰው ለኀጢአት መቅጫ ብቻ ሳይሆን ለመንፈሳዊ ሕይወት ዕድገትና ለእምነት ጽናት ስለ ሚጠቅም ነው (5፥17፤ ዘዳ 8፥5፤ 2ሳሙ 7፥14፤ መዝ 94፥12፤ ምሳ 3፥11-12፤ 1ቆሮ 11፥32፤ ዕብ 12፥5-11 ይመ)።

2፥11 ***ሦስቱ... ወዳጆች፤*** በዕድሜ ከኢዮብ ይበልጣሉ (15፥10 ይመ)። ***ኤልፋዝ፤*** ኤዶማዊ ስም ነው (ዘፍ36፥11 ይመ)። ***ቴማናዊው፤*** ቴማን ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ የሚገኝ የኤዶም መንደር ነበር (ዘፍ 36፥11፤ ኤር 49፥7፤ ሕዝ 25፥13፤ አሞ 1፥12፤ አብ 9 ይመ)። ***ሹሐዊው፤*** በልዳዶስ የአብርሃምና የኬጡራ የመጨረሻ ልጅ የሱዌሕ ዘር ሳይሆን አይቀርም (ዘፍ 25፥2)። ***ናዕማታዊው፤*** ከ11፥1፤ ከ20፥1፤ 42፥9 በስተቀር በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በየትኛውም ቦታ የማይገኝ ስም ነው።

2፥12 ***እርሱ መሆኑን ሊለዩ አልቻሉም፤*** ከኢሳ 52፥14፤ 53፥3 ጋር ያነጻጽሩ። ***ልብሳቸውንም ቀደው በራሳቸው ላይ ትቢያ ነሰነሱ፤*** በገሀድ የሚታይ የሐዘን ምልክት ነው (የ1፥20 ማብ ይመ)።

2፥13 ***ከእርሱ ጋር መሬት ላይ ተቀመጡ፤*** የሚበጅ ዐይ ነት ነው የሚባል ማጽናኛ ቃል ነው፤ ሕዝ3፥15 ይመ። ***ሰባት፤*** ዘፍ 50፥10፤ 1ሳሙ 31፥13 ይመ፤ ፍጹምነትን የሚያመለክት ቍጥር ነው፤ (1፥2 እንዲሁም የሩት 4፥15 ማብ ይመ)። ***አንዳች ቃል የተናገረው አልነበረም፤*** የሚበጅ ምክር ነው ተብሎ ከእነ ርሱ ከተሰነዘረው ቃል ይልቅ፣ እንዲሁ አጠገቡ መቀመጣቸው ራሱ የሚያጽናና ነበር (16፥2-3 ይመ)።

*3፥11* መግቢያ የሆኑት የመጀመሪያዎቹ ሁለት ምዕራፎች ስድ ንባብ ናቸው፤ ከዚህም ምዕራፍ ጀምሮ ግን ረጅም የግጥም ጽሑፍ ይቀጥላል (3፥1-42፥6)፤ ማጠቃለያውም ስድ ንባብ ነው (42፥7-17)።

3፥3 ***የተወለድሁበት ቀን... ይጥፋ፤*** ኢዮብ ከእግዚአብሔር ምሕረት የተነሣ መኖር በመቻሉ ሐሤት ቢያደርግም፣ አሁን ግን ከሚቋቋመው በላይ ሆኖበታል፤ እግዚአብሔርን ለማማረር ፈልጎ ነበር፤ ሆኖም ግን አላደረገውም።

3፥4 ***ጨለማ ይሁን፤*** እግዚአብሔር በዘፍ1፥3 ላይ "ብርሃን ይሁን" ብሎ ነበር፤ ኢዮብ ግን ተመሳሳይ ቋንቋ ይጠቀ ምና የእግዚአብሔርን ሥራ ይቃወማል።

3፥8 ***ቀንንም የሚረግሙ፤*** ልክ እንደ በለዓም (ዘኍ 22-24) የምሥራቅ ኮከብ ቈጣሪዎች በሰዎች፣ በነገሮችና በቀኖች ላይ የርግማን ናዳ ያወርዳሉ። ***ሌዋታንን፤*** ኢዮብ ግልጽና ዘይቤያዊ በሆነ ንግግር ቀናትን የሚረግሙ ሁሉ የተወለደበትን ቀንና ሌሊት ይውጥለት ዘንድ የባሕር አውሬ የሆነውን ሌዋታንን እንዲያነሣሡለት ይመኛል (የኢሳ 27፥1 ማብ ይመ)።

*3፥11-12፡16፡20-23፤* መልስ አዘል ተከታታይ ጥያቄዎች ናቸው።

[16]ወይም እንደ ተቀበረ ጭንጋፍ
ብርሃንም እንዳላየ ሕፃን በሆንሁ ነበር።
[17]በዚያ ክፉዎች ማወካቸውን ይተዋሉ፤
ደካሞችም በዚያ ያርፋሉ፤
[18]ምርኮኞች እንደ ልባቸው ይቀመጣሉ፤
ከአንገዲህም የአስጨናቂዎቻቸውን
ጩኸት አይሰሙም።
[19]ትንሹም ትልቁም በዚያ ይገኛል፤
ባሪያው ከጌታው ነጻ ወጥቶአል።

[20]"በመከራ ላሉት ብርሃን፣
ነፍሳቸው ለተማረረች ሕይወት ለምን
ተሰጠ?
[21]ሞትን በጉጉት ለሚጠብቁና ለማያገኙት፣
ከተሰወረ ሀብት ይልቅ ለሚሹት፣
[22]ወደ መቃብር ሲቃረቡ ደስ እያላቸው፣
በሐሤት ለሚሞሉ ሕይወት ለምን
ተሰጠ?
[23]መንገዱ ለተሰወረበት ሰው፤
እግዚአብሔርም በዐጥር ላጠረው፣
ሕይወት ለምን ተሰጠ?
[24]ትካዜ ምግብ ሆኖኛልና፤
የሥቃይ ጩኸቴም እንደ ውሃ ይፈሳል።
[25]የፈራሁት ነገር መጥቶብኛል፤
የደነገጥሁበትም ደርሶብኛል።
[26]ሰላም የለኝም፤ ርጋታም የለኝም፤
ሁከት እንጂ ዕረፍት የለኝም"

**ኤልፋዝ**

**4** [1]ቴማናዊው ኤልፋዝም እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"አንድ ሰው ከአንተ ጋር ለመናገር
ቢሞክር፣ ቅር ይልሃልን?
ጸሩ ግን ከመናገር ማን ሊቈጠብ
ይችላል?
[3]እነሆ፤ አንተ ብዙዎችን ታስተምር እንደ
ነበር አስብ፤
የደከሙትንም እጆች ታበረታ ነበር፤
[4]ቃልህ የተሰናከሉትን ያነሣ ነበር፤
የሚብረከረከውንም ጒልበት ታጸና
ነበር።
[5]አሁን ግን መከራ አገኘህ፣ አንተም ተስፋ
ቈረጥህ፤
ሸንቈጠህ፤ ደነገጥህም።
[6]እግዚአብሔርን መፍራት መታመኛህ
ቀና አካሄድህም ተስፋህ አይደለምን?
[7]"አሁንም አስተውል፤ ንጹሕ ሆኖ የጠፋ፣
ማን ነው?
ቅኖችስ መች ተደምስሰው ያውቃሉ?
[8]እኔ እንዳየሁ፣ ክፋትን የሚያርሱ፣
መከራንም የሚዘሩ ያንኑ ያጭዳሉ።
[9]በእግዚአብሔር እስትንፋስ ይጠፋሉ፤
በቍጣውም ወላፈን ይደመሰሳሉ።
[10]አንበሳ ያገሣል፤ ቍጣውም አንበሳ
ይጮኻል፤
የደቦል አንበሳው ጥርስ ግን
ተሰብሮአል።
[11]ብርቱው አንበሳ አደን በማጣት
ይሞታል፤
የአንበሳዪቱም ግልገሎች ይበተናሉ።
[12]"ቃል በምስጢር መጣልኝ፤
ጆሮዬም ሹክሹክታውን ሰማች።
[13]በሚያስጨንቅ የሌሊት ሕልም ውስጥ፣
ከባድ እንቅልፍም በሰዎች ላይ በወደቀ
ጊዜ፣
[14]ፍርሀትና መንቀጥቀጥ ያዘኝ፤
ዐጥንቶቼም ሁሉ ተናወጡ።

3፥16 ቍ31፤መዝ 58፥8፤71፥6፤መክ4፥3፤6፥3
3፥17 ቍ13፡26፤ ኢዮ30፥26፤መክ4፥2፤ኢሳ14፥3
3፥18 ዘፍ15፥13፤ ኢዮ39፥7፤ኢሳ51፥14
3፥19 ኢዮ9፥22፤ 17፥16፤21፥33፤24፥24፤30፥23፤መክ12፥5
3፥20 1ሳሙ1፥10፤ሕዝ27፥30-31
3፥21 መዝ119፥127፤ምሳ2፥4፤ራእ9፥6
3፥22 ኢዮ7፥16፤ መክ4፥3፤ኤር8፥3
3፥23 ኢዮ6፥4፤16፥13፤19፥12፤መዝ88፥8፤ምሳ4፥19፤ኢሳ59፥10፤ኤር13፥16፤23፥12፤ሰቆ2፥4፤3፥7፤ ሆሴ2፥6
3፥24 1ሳሙ1፥15፤ ኢዮ6፥7፤30፥16፤33፥20፤መዝ5፥1፤6፥6፤22፥14፤32፥3፤38፥8፡9፤42፥3፡4፤80፥5፤107፥18፤ኢሳ35፥10፤53፥12፤ሰቆ2፥12
3፥25 ዘፍ42፥36፤ ኢዮ7፥9፤9፥28፤30፥15፤ሆሴ13፥3
3፥26 ቍ17፤ኢዮ 7፥4፡14፤10፥18፤19፥8፤መዝ6፥6፤ኢሳ48፥22፤ዳን4፥5፤ማቴ11፥28፤ዮሐ14፥27
4፥1 ዘፍ36፥11፤ኢዮ 15፥1፤22፥1
4፥2 ኢዮ32፥20፤ ኤር4፥19፤20፥9
4፥3 ዘዳ32፥2፤ኢዮ 26፥2፤29፥23፤መዝ 71፥9፤ኢሳ13፥7፤35፥3፤ሆሴ6፥3፤ሶፎ3፥16፤ ዕብ12፥12
4፥4 ኢዮ16፥5፤29፥11፡15፡16፡25፥፤ኢሳ 1፥17፤35፥3፤ኤር31፥8፤ዕብ12፥12
4፥5 ኢሱ1፥9፤ሩት 1፥13፤ኢዮ1፥11፤ 6፥14፤19፥21፤30፥21፤መዝ38፥2፤ምሳ24፥10፤ኢሳ53፥4 4፥6 ዘፍ6፥9፤25፥18፥19፤መዝ27፥3፤71፥5፤ምሳ3፥26 4፥7 ኢዮ5፥11፤8፥20፤ 3፡6፥7፤መዝ37፥25፤41፥12፤91፥9-10፤ምሳ12፥21፤19፥23፤2ጴጥ2፥9
4፥8 ምሳ14፥18፤ኢዮ5፥3፥6፤15፥17፡35፤መዝ7፥14፡15፤9፥15፤ምሳ 11፥18፤22፥8፤ኢሳ17፥11፤59፥4፤ሆሴ8፥7፤10፥13፤ገላ6፥7-8 4፥9 ዘፀ15፥10፤ዘሌ26፥38፤ኢዮ41፥21፤40፥13፤ኢሳ25፥7፤2ተሰ2፥8
4፥10 ኢዮ5፥15፤29፥17፤36፥6፤38፥15፤መዝ17፥12፤22፥13፡21፤ 35፥10፤58፥6፤ምሳ28፥15 4፥11 ዘዳ28፥41፤ኢዮ5፥4፤27፥14፤29፥17፤ መዝ34፥10፤58፥6፤ምሳ30፥14 4፥12 ቍ17፡21፤ኢዮ26፥14፤ 32፥13፤33፥14፤ኤር9፥23 4፥13 ኢዮ33፥15 4፥14 ኢዮ21፥6፤ መዝ48፥6፤55፥5፤119፥120፡161፤ኤር5፥22፤23፥9፤ዳን10፥8፤ዕን3፥16፤2ቆሮ7፥15

*3፥16፤* ኢዮብ ከተወለደ በኋላ ሆኖበት እንጂ ሞቶ መወለዱን ይመኝ ነበር፤ ምክንያቱም የሰላምና የዕረፍት ስፍራ (ቍ 13-19፤ የዘፍ 37፥35 ይመ) ብሎ ባሰበው በመቃብር (በሲኦል) በኖረ ነበርና፤ ስፍራውም ሰላምና ዕረፍት ከሌለበት (ቍ 26) ከአሁኑ ከእርሱ ሁኔታ በእጅጉ ይሻል ነበርና።

3፥18 *የአስጨናቂዎቻቸውን ጩኸት፤* በግብፅ እንደነበረው ሁኔታ ማለት ነው (ዘፀ 5፥13-14 ይመ)።

*3፥21-22፤* ኢዮብ ሞትን ከልቡ ፈልጎአል።

3፥23 *እግዚአብሔርም በዐጥር ላጠረው፤* በዙሪያው ቅጥር ያደረገለት አምላክ (1፥10 እና ማብ ይመ)፣ አሁን ግን በሁከት እንዲከበብ ያደረገው ያህል ተሰማው (ቍ 26 ይመ)።

4፥1 *ቴማናዊው ኤልፋዝም፤* የ2፥11 ማብ ይመ። ቴማን በጥበብ የታወቀች የኤዶም ከተማ ነበረች (ኤር 49፥7 ይመ)። የሦስቱ የኢዮብ ጓደኞች ንግግር እውነትን ያዘለ ቢሆንም፣ በዐውዱ መሠረት በጥንቃቄ ሊታይ ይገባል። የኢዮብ ወዳጆች ሥቃይ ስለ ደረሰበት ወዳጃቸው፣ የሚያውቁት ብዙ ነገር አለ፤ እግዚአብሔር፣ ኢዮብ በሰይጣን እንዲፈተን ሲፈቅድ ምን ዐላማ እንደ ነበረው አለማወቃቸው ግን፣ በኢዮብ ላይ ተደራቢ ችግር ፈጥሮበት ነበር።

4፥2 *ለመናገር ቢሞክር፤* ኤልፋዝ ስለ ኢዮብ ደኅንነት የሚጨነቅ ይመስላል፤ ከዚህም የተነሣ ብርታት ሊሰጥ የሚችል የማጽናኛ ቃል አሰማው (ቍ 3-4)። *ቅር ይልሃልን?* የ9፥23 ማብ ይመ።

4፥5 *መከራ አገኘህ፤* 1፥11፤ 2፥5፤ 19፥21 ይመ።

*4፥6-7፤* ኢዮብ ልበ ሙሉ እንዲሆን፣ እግዚአብሔርን መፍራቱ በእግዚአብሔር ዘንድ ዋጋ እንደሚኖረው፣ ለተላላፊነቸው አንዳንድ ነገሮች እግዚአብሔር አሁን ቢቀጣውም፣ በመጨረሻው ግን የሚያምር እንደሚሆን (ቍ 17፥5፥17 ይመ)፣ ጌታ ከክፉዎች ጋር እንደማይቀጣው እርግጠኛ ይሆን ዘንድ ኤልፋዝ መከረው።

4፥6 *እግዚአብሔርን መፍራት፤* የ1፥1 ማብ ይመ። ይህን ቃል የተጠቀመው ኤልፋዝ ብቻ ነው (15፥4፤ 22፥4 ይመ)።

*4፥7-9፤* ኢዮብ በእውነት ንጹሕ ሰው ከሆነ አይጠፋም።

*4፥8-11፤* እጅግ ጠንካራ የሆኑ አንበሶች እንኳ በመጨረሻ እንደሚሞቱ ክፋዎችም በመጨረሻ ይጠፋሉ (ቍ 8-9)።

4፥9 *በቍጣውም ወላፈን፤* ዘጸ 15፥7-8 ይመ፤ የእግዚአብሔር ቍጣ በጣም የሚያስፈራ ነው።

*4፥12-21፤* ኤልፋዝ በሕልሙ ያየውን ምስጢራዊ ልምምድ (ቍ 13 ይመ)፣ በዚህም አማካይነት መጣልኝ የሚለውን ራእይና በዚሁ ላይ የመሠረተውን ለኢዮብ የሚሰጠውን ምክሩን ጠጒር የሚያቆም (ቍ 15 ይመ) ይለዋል።

4፥13 *የሌሊት ሕልም ውስጥ፣ ከባድ እንቅልፍም በሰዎች ላይ በወደቀ ጊዜ፤* በ33፥15 ላይ የኤልፋዝ ቃል በኤሊሁ ተደግሞ ይገኛል።

4፥14 *ዐጥንቶቼም ሁሉ ተናወጡ፤* ተስፋ የመቍረጥ ምልክት ነው (ኤር 23፥9፤ ዕብ 3፥16 ይመ)።

[15]መንፈስ ሽው ብሎ በፊቴ አለፈ፤
የገላዬም ጠጕር ቆመ።
[16]እርሱም ቆመ፣
ምን እንደ ሆነ ግን መለየት አልቻልሁም፤
አንድ ቅርጽ በዐይኔ ፊት ነበረ፤
በእርጭታ ውስጥ እንዲህ የሚል ድምፅ ሰማሁ፤
[17]‘ሥጋ ለባሽ ከእግዚአብሔር ይልቅ ጻድቅ ሊሆን ይችላልን?
ሰውስ ከፈጣሪው ይልቅ ንጹሕ ሊሆን ይችላልን?
[18]እግዚአብሔር በአገልጋዮቹ ላይ እምነት ካልጣለ፣
መላእክቱንም በስሕተታቸው ከወቀሰ፤
[19]ይልቁንስ በጭቃ ቤት የሚኖሩ፣
መሠረታቸው ከዐፈር የሆነ፣
ከብልም ይልቅ በቀላሉ የሚጨፈለቁ እንዴት ይሆኑ?
[20]በንጋትና በምሽት መካከል ይደቃሉ፤
ሳይታሰብም ለዘላለም ይጠፋሉ።
[21]ያለ ጥበብ ይሞቱ ዘንድ፣
የድንኳናቸው ገመድ አልተነቀለምን?[ሀ]

5 “እስቲ ተጣራ፤ የሚመልስልህ አለን?
ከቅዱሳንስ ወደ ማንኛው ዘወር ትላለህ?
[2]ሞኙን ሰው ብስጭት ይገድለዋል፤
ቂሉንም ቅናት ያጠፋዋል።
[3]ቂል ሰው ሥር ሰዶ አየሁት፤
ግን ድንገት ቤቱ ተረገመ።
[4]ልጆቹ የኑሮ ዋስትና የራቃቸው፤
በፍርድ አደባባይ ጥቃት የደረሰባቸው፣
ታዳጊ የሌላቸው ናቸው።
[5]ከእሾህ መካከል እንኳ አውጥቶ፤
ራብተኛ ሰብሉን ይበላበታል፤
ጥማተኛም ሀብቱን ይመኝበታል።
[6]ችግር ከምድር አይፈልቅም፤
መከራም ከመሬት አይበቅልም።
[7]ፍንጣሪው ከእሳቱ ላይ ሽቅብ እንደሚወረወር፣
ሰውም ለመከራ ይወለዳል።
[8]“እኔ ብሆን ኖሮ፣ ወደ እግዚአብሔር በቀረብሁ፣
ጒዳዬንም በፊቱ በገለጽሁለት ነበር።
[9]እርሱ፣ የማይመረመሩ ድንቅ ነገሮች፣
የማይቈጠሩም ታምራት ያደርጋል።
[10]ምድሪቱን በዝናብ ያረሰርሳል፤
ሜዳውንም ውሃ ያጠጣል።
[11]የተዋረዱትን በከፍታ ቦታ ያስቀምጣል፤
ያዘኑትንም ወደ አስተማማኝ ስፍራ ያወጣቸዋል።
[12]እጃቸው ያሰቡትን እንዳይፈጽም፣
የተንኰለኞችን ዕቅድ ያከሽፋል።
[13]ጠቢባንን በጥበባቸው ይይዛል፤
የተንኰለኞችንም ሤራ ያጠፋል።
[14]ቀኑ ጨለማ ይሆንባቸዋል፤
በቀትርም ጊዜ በሌሊት እንዳለ ሰው በዳበሳ ይሄዳሉ።
[15]ችግረኛውን ከአፋቸው ሰይፍ፣
ከኀይለኛውም እጅ ያድነዋል።
[16]ስለዚህ ድኻ ተስፋ አለው፤
ዐመፅም አፏን ትዘጋለች።

4፥15 ዳን5፥6፤7፥15፤28፤10፥8፤ማቴ14፥26
4፥16 1ነገ19፥12
4፥17 ኢዮ8፥3፤9፥2፤10፥3፤13፥8፤14፥4፤15፥14፤21፥14፤25፥4፤31፥15፤32፥22፤35፥10፤36፥3፡13፤37፥23፤40፥19፤መዝ18፥26፤51፥5፤119፥73፤143፥2፤ምሳ20፥9፤መክ7፥20፤ኢሳ51፥13፤ሚል2፥10፤ሐሥ17፥24
4፥18 ኢዮ15፥15፤21፥22፤25፥5፤ዕብ1፥14
4፥19 ዘፍ2፥7፤ኢዮ5፥4፤7፥17፤10፥9፤15፥16፤17፥14፤22፥16፤25፥6፤33፥6፤መዝ22፥6፤ኢሳ41፥14፤64፥8፤ሮሜ9፥21፤2ቆሮ4፥7፤5፥1
4፥20 ኢዮ14፥2፡20፤15፥33፤20፥7፤24፥24፤መዝ89፥47፤90፥5-6፤ያዕ4፥14
4፥21 ኢዮ8፥22፤18፥21፤36፥12፤ምሳ5፥23፤ኢሳ38፥12፤ኤር9፥3፤ዮሐ8፥24
5፥1 ኢዮ15፥15፤መዝ89፥5፡7፤ዕን1፥2
5፥2 ኢዮ21፥15፤36፥13፤ምሳ12፥16፤ገላ5፥26
5፥3 ኢዮ4፥8፤24፥18፤መዝ37፥22፡35-36፤109፥9-10፤ምሳ3፥33፤6፥15፤ኢሳ40፥24፤ኤር12፥2፤ሕዝ17፥6
5፥4 ኢዮ4፥11፡19፤20፥10፤27፥14፤መዝ109፥12፤ኢሳ9፥17፤አሞ5፥12፤1ዮሐ2፥1
5፥5 ዘሌ26፥16፤መሳ2፥15፤ኢዮ20፥18፤31፥8፤ሚክ6፥15
5፥6 ኢዮ4፥8
5፥7 ዘፍ3፥17፤ኢዮ10፥17፤15፥35፤ መዝ51፥5፤58፥3፤90፥10፤ምሳ22፥8 5፥8 ኢዮ8፥5፤11፥13፤13፥3፡15፤23፥4፤40፥1፤መዝ35፥23፤50፥15፤ኤር12፥1፤1ቆሮ4፥4 5፥9 ዘዳ29፥29፤ኢዮ9፥4፡10፤11፥7፤25፥2፤26፥14፤33፥12፤36፥5፡22፡26፤37፥5፡14፡16፡23፤42፥3፤መዝ40፥5፤71፥15፡17፤72፥18፤78፥4፤111፥2፤131፥1፤139፥6፡17፤145፥3፤ኢሳ40፥28፤ሮሜ11፥33 5፥10 ዘሌ26፥4፤ኢዮ36፥28፤37፥6፡13፤38፥28፡34፤መዝ135፥7፤ኤር14፥22፤ማቴ5፥45 5፥11 1ሳሙ2፥7-8፤ኢዮ4፥7፤መዝ75፥7፤113፥7-8፤ኢሳ61፥2፤ማቴ5፥4፤23፥12፤ሮሜ12፥15፤ያዕ4፥10 5፥12 ነህ4፥15፤ኢዮ12፥23፤መዝ33፥10፤78፥59፤140፥8፤ኢሳ8፥10፤19፥3፤ኤር19፥7 5፥13 ኢዮ9፥4፤15፥5፤18፥7፤37፥24፤መዝ36፥3፤ምሳ21፥30፤29፥6፤ኢሳ29፥14፤44፥25፤ኤር8፥8፡9፤18፥18፤51፥57፤ሉቃ20፥23፤1ቆሮ3፥19፤2ቆሮ11፥3፤ኤፌ4፥14 5፥14 ዘዳ28፥29፤ኢዮ15፥22፡30፤18፥5፡6፡18፤20፥26፤22፥11፤27፥20፤ኢሳ8፥22፤አሞ8፥9፤ዮሐ12፥35 5፥15 ዘፀ22፥23፤ኢዮ4፥10፤8፥6፤22፥27፤31፥22፤33፥26፤36፥15 5፥16 ኢዮ20፥19፤31፥16፤መዝ63፥11፤107፥42፤ምሳ17፥5፤22፥22፤ኢሳ11፥4፤41፥17፤61፥1፤ሮሜ3፥19

[ሀ]21 አንዳንድ ተርጓሚዎች ቍ 17 ላይ ያቆማሉ

*4፥17-21፤ ሥጋ* ለባሽ ሁሉ ኀጢአተኛ ነው፤ ስለዚህ እግዚአብሔር ሊቀጣቸው ይገባል። ኢዮብም እግዚአብሔር ስለ ቈነጠጠው እግዚአብሔርን ማመስገኑ ተገቢ ነው (5፥17 ይመ)።

*4፥18-19፤* ከዐፈር ያልተሠሩት የሰማይ መላእክት በእግዚአብሔር ፊት በደለኞች ከሆኑ ሰውማ ምንኛ በደለኛ ነው (15፥15-16 ይመ)።

4፥18 *በአገልጋዮቹ፤* መላእክት ናቸው።

4፥19 *በጭቃ ቤት፤* ከዐፈር የተሠራውን ሰውነት ያመለክታል (10፥9፤ 33፥6፤ እንዲሁም የዘፍ 2፥7 ማብ ይመ)። *ከብልም፤* ሰው በቀላሉ እንደ ሸክላ ሊሰበር የሚችል መሆኑን የሚያሳይ ነው።

4፥20 *በንጋትና በምሽት መካከል፤* ሕይወት ምን ያህል አጭር እንደ ሆነች የሚያመለክት ነው።

4፥21 *የድንኳናቸው፤* ልክ እንደ ሰው አካል ጊዜያዊ መኖሪያ ነው (2ቆሮ 5፥1፡4፤ 2ጴጥ 1፥13 ይመ)። *ያለጥበብ፤* ፍላጎት አልባና ስሜት አልባ (ቍ 20 ይመ)።

5፥1 *ወደ ማንኛው ዘወር ትላለህ?* ጒዳይህን ለእግዚአብሔር ለመንገር ለማለት ነው፤ በእግዚአብሔርና በኢዮብ መካከል ገብቶ የመሸምገል ተግባር የመጽሐፉ አስፈላጊው መልእክት ነው (9፥33፤ 16፥19-20 ይመ)። *ከቅዱሳንህ፤* በመግቢያው ላይ እንደ ተመለከተው “የእግዚአብሔር ልጆች” የተባሉት ቅዱሳን መላእክት ናቸው (በ1፥6 እና 2፥ ላይ በአማራጭ የቀረበውን ማብ ይመ)።

*5፥2፤* ኢዮብ እግዚአብሔርን እንደ ጠላና እግዚአብሔርን መጥላት ደግሞ መቀሠፍን እንደሚያስከትል ኤልፋዝ እንዲሁ በደፈናው ይናገራል። *ቂሉንም፤* የእግዚአብሔር ነገር የሌለው ወይም ደንታ ቢስ ማለት ነው (በ2፥10 እና ምሳ 1፥7 ላይ በአማራጭ የቀረበውን ማብ ይመ)።

5፥3 *ቂል ሰው ሥር ሰዶ፤* ክፉ ሰው ሥር እንደሰደደ ዛፍ ለምልሞ ማለት ነው።

*5፥6፤* ችግር እንደ አረም ዝም ብሎ የሚበቅል ሳይሆን፣ ሆን ተብሎ ተዘርቶ በእንክብካቤ የሚያድግ ነው።

5፥7 *ሰውም ለመከራ ይወለዳል፤* 14፥1 ይመ። ማንም ሰው በእግዚአብሔር ፊት ጻድቅ እንዳልሆነ ይህ ማረጋገጫ ነው (4፥17-19 ይመ)፤ ኢዮብ የደረሰበትን መከራ በትግዕሥት በመቀበል (ቍ 1-7 ይመ)፣ በትሕትና መጓዝ ነበረበት፤ ይህም የእግዚአብሔርን በረከት ያስገኛል፤ ኢፍትሐዊነትም ቦታ አይኖረውም (ቍ 16)። *ፍንጣሪው፤* በቁሙ፣ “የሬሼፍ ልጆች” ማለት ነው። በከነዓናውያን እምነት ሬሼፍ የቸነፈርና የጥፋት አምላክ ነው። በብሉይ ኪዳን “የሬሼፍ ልጆች” የሚለው ሐረግ፣ ቅኔያዊ ምስል ለመፍጠር ሲባል፣ እሳት (ማሕ 8፥6)፣ የነጐድጓድ ችቦ (መዝ 78፥48)፣ አስቃቂ በሽታ (ዘዳ 32፥24፣ ዕን 3፥5) ተብሎአል።

*5፥9፤* በ9፥10 ላይ ተደግሞአል።

*5፥13፤* በ1ቆሮ 3፥19 ላይ በከፊል ተጠቅሶአል፤ ይህም በአዲስ ኪዳን ውስጥ የኢዮብ መጽሐፍ በግልጽ የተጠቀሰበት ብቸኛ ስፍራ ነው።

[17]"እነሆ፣ እግዚአብሔር የሚገሥጸው ሰው
ምስጉን ነው፤
ስለዚህ ሁሉን የሚችለውን[*] አምላክ
ተግሣጽ አትናቅ።
[18]እርሱ ያቈስላል፣ ይፈውሳል፤
እርሱ ይሰብራል፤ በእጁም ይጠግናል፤
[19]እርሱ ከስድስት መቅሠፍት ይታደግሃል፤
በሰባተኛውም ጉዳት አያገኝህም።
[20]በራብ ጊዜ ከሞት፣
በጦርነትም ከሰይፍ ያድንሃል።
[21]ከምላስ ጅራፍ ትሰወራለህ፤
ጥፋት ሲመጣም አትፈራም።
[22]በጥፋትና በራብ ላይ ትሥቃለህ፤
የምድርንም አራዊት አትፈራም።
[23]ከሜዳ ድንጋዮች ጋር ትዋዋላለህና፤
የዱር አራዊትም ከአንተ ጋር
ይስማማሉ።
[24]ድንኳንህ በሚያስተማምን ሁኔታ እንዳለ
ታውቃለህ፤
በረትህን ትቃኛለህ፤ አንዳችም
አይጐድልብህም።
[25]ዘሮችህ አያሌ እንደሚሆኑ፣
የምትወልዳቸውም እንደ ሣር
እንደሚበዙ ታውቃለህ።
[26]የእህል ነዶ ጉምርቶ በወቅቱ
እንደሚሰበሰብ፣
ዕድሜ ጠግበህ ወደ መቃብር ትሄዳለህ።
[27]"እነሆ፤ ይህን ሁሉ መርምረናል፤ እውነት
ሆኖ አግኝተነዋል
ስለዚህ ልብ በል፤ ተቀበለውም።"

## ኢዮብ

**6** ኢዮብም እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"ምነው ሐዘኔ በተመዘነ!
መከራዬም ሚዛን ላይ በተቀመጠ!
[3]ከባሕር አሸዋ ይልቅ በከበደ፣
ኀይለ ቃሌም ባላስገረመ ነበር!
[4]ሁሉን የሚችል አምላክ ፍላጻ በውስጤ
ነው፤
መንፈሴም መርዙን ትጠጣለች፤
የእግዚአብሔር ማስደንገጥ ተሰልፎብኛል።
[5]የሜዳ አህያ ሣር እያለው፣
በሬስ ድርቆሽ እያለው፣ ይጮኻልን?
[6]የማይጣፍጥ ምግብ ያለ ጨው ይበላልን?
ወይስ የዕንቍላል[a] ውሃ ጣዕም አለውን?
[7]እንዲህ ዐይነቱን ምግብ እጸየፋለሁ፤
ለመንካትም አልፈልግም።
[8]"ምነው ልመናዬ በተመለሰልኝ፤
እግዚአብሔር የምመኘውን በሰጠኝ
[9]እግዚአብሔር አድቅቆ ያጠፋኝ ዘንድ፣
ምነው እጁ በተፈታ!
[10]ፋታ በማይሰጥ ሕመም ውስጥ
እየተደሰትሁ፣
ይህ መጽናኛ በሆነልኝ ነበር፤
የቅዱሱን ትእዛዝ አልጣስሁምና።
[11]"አሁንም ተስፋ አደርግ ዘንድ ብርታቴ፣
እታገሥስ ዘንድ አለኝታዬ ምንድን ነው?
[12]የድንጋይ ጉልበት አለኝን?
ሥጋዬስ ናስ ነውን?
[13]ያልተሳካልኝ ሰው ነኝና፣
ራሴን ለመርዳት ምን ጉልበት አለኝ?

5፥17 ዘፍ17፥1፤ዘጸ 8፥5፤ኢዮ15፥11፤33፥19፤36፥10፤መዝ94፥12፤ምሳ3፥11፤ኤር31፥18፤ሰቆ3፥7፤ዕብ12፥5-11፤ያዕ1፥12
5፥18 ዘዳ32፥39፤ መዝ147፥3፤ኢሳ57፥15፤61፥1፤ሆሴ6፥1
5፥19 መዝ34፥19፤ 91፥10፤ምሳ3፥25-26፤ 24፥15-16፤ዳን3፥17፤ 6፥16
5፥20 ቍ 22፤መዝ 22፥20፤33፥19፤37፥19፤91፥7፤140፥7፤ 144፥10፤ኤር39፥18
5፥21 ቍ 15፤መዝ12፥2-4፤ 23፥4፤27፥3፤11፥20፤ 91፥5
5፥22 ቍ 20፤ዘሌ 25፥18፤ኢዮ8፥21፤ 39፥7፡18፡22፤41፥29፤ መዝ91፥13፤ሆሴ2፥ 18፤ማር1፥13
5፥23 2ነገ3፥19፡ 25፤ኢዮ40፥20፤መዝ 91፥12፤ኢሳ11፥6-9፤ 28፥15፤65፥25፤ሕዝ 34፥25፤ሆሴ2፥18፤ ማቴ13፥8
5፥24 ኢዮ8፥6፤12፥ 6፤21፥9፤22፥23
5፥25 ዘዳ28፥4፤ መዝ72፥16፤112፥ 2፤ኢሳ44፥3፡4፤48፥19
5፥26 ዘፍ15፥15፤ ዘጸ11፥21፤መክ8፥13፤ ምሳ3፥21-26
5፥27 ኢዮ8፥5፤11፥ 13፤22፥27፤32፥10፡ 17
6፥2 ኢዮ31፥6፤ምሳ 11፥1፤ዳን5፥27
6፥3 ቍ 11፡26፤ 1ነገ4፥29፤ኢዮ7፥11፤ 16፥6፤21፥4፤23፥2፤ ምሳ27፥3
6፥4 ዘፍ17፥1፤ዘጸ 32፥23፡32፤ ኢዮ3፥23፤ 7፥20፤9፥34፤13፥21፤16፥12፡13፤18፥11፤19፥12፤21፥20፤ 23፥6፤27፥20፤30፥15፡21፤33፥16፤34፥6፤መዝ38፥2፤88፥15-18፤ኤር 15፥18፤30፥12፤ሰቆ3፥12 6፥5 ዘፍ16፥12፤ኢዮ24፥6፤30፥7፤ኢሳ30፥24 6፥6 ኢዮ33፥20፤መዝ107፥18 6፥7 ኢዮ3፥24 6፥8 ኢዮ 14፥13 6፥9 ዘኍ11፥15፤ኢዮ19፥21፤መዝ31፥22 6፥10 ዘሌ11፥44፤2ነገ19፥22፤ኢዮ2፥11፤15፥11፤22፥22፤23፥12፤መዝ38፥17፤ 94፥19፤119፥102፤ኢሳ31፥1፤ኤር4፥19፤45፥3፤ማር8፥38 6፥11 ቍ 3 6፥12 ኢዮ26፥2 6፥13 ኢዮ26፥2

[*]17 በዕብራይስጥ ሻዳይ ማለት ሲሆን በዚህ ቍጥርና በኢዮብ መጽሐፍ ውስጥ እንዲሁ ነው
[a]6 በዕብራይስጥ የዚህ ሐረግ ትርጕም አይታወቅም

*5፥17-26፤* ቀደም ያለው መዝሙር (8-16) የእግዚአብሔርን ቸርነትና ትክክለኛነት የሚያወሳ ሲሆን፣ ይህኛው ቅኔ ደግሞ እግዚአብሔር የሚቀጣው ሰው (ምሳ 1፥2፡7፤ 3፥12፤ 23፥13፡23) ምን ያህል የተባረከ እንደ ሆነ ያመለክታል። ኤልፋዝ ቅጣቱ ለጊዜው እንደ ሆነና ተከትሎት የሚመጣው ግን በጎ ነገር መሆኑን (ቍ 18)፣ በጎ የሆነውም ሰው ምን ጊዜም ከጥፋት እንደሚድን ተናገረ። ይሁን እንጂ ኢዮብ ሀብቱንና ልጆቹን አጥቶ ሳለ፣ በዚህ ጊዜ ያለ ሥጋት ተጠብቆ ስለ መኖርና (ቍ 24) ስለ ልጆች (ቍ 25) መወሳቱ፣ እርሱን ለመጕዳት ሆን ተብሎ የተሰነዘረ የጨካኝ ሰው ሐሳብ ሳይመስለው አልቀረም።

5፥17 *ሁሉን የሚችለውን አምላክ፤* በዕብራይስጥ ኤልሻዳይ (ዘፍ17፥1) ማለቱ ነው። በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ሠላሳ አንድ ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን፣ ይህ የመጀመሪያው ነው።

*5፥18-19፤* ሆሴ 6፥1-2 ይመ።

5፥19 *ከስድስት... በሰባተኛውም፤* 33፥29፤ 40፥5፤ ምሳ 6፥16፤ 30፥15፡18፡21፡29፤ መክ 11፥2፤ አሞ 1፥3፡6፡9፡11፡13፤ 2፥1፡4፡6፤ ሚክ 5፥5 ይመ። አብዛኛውን ጊዜ ቍጥሮች በዚህ ዐይነት መልክ በቅደም ተከተል ሲቀመጡ ቃል በቃል እንዲተረጐሙ ሳይሆን፣ ብዛትን እንዲያሳዩ ተብሉ ነው።

5፥23 *ድንጋዮች ጋር ትዋዋላለህና፤* ድንጋዮች እንኳ ከአንተ ጋር ሰላም ይኖራቸዋል፤ በማሳህ ላይ ያለውን እህልህን አያበላሹብህም ለማለት የገባ ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው (2ነገ 3፥19፤ ኢሳ 5፥2፤ ማቴ 13፥5 ይመ)።

5፥25 *እንደ ሣር፤* ቍጥሩ እንደ ሣር ቅጠል የበዛ ማለት ነው (የዘፍ 13፥16 ማብ ይመ)።

*5፥26፤* የኤልፋዝ ትንበያ እርሱ ከሚያስተውለው በላይ ትክክል ነው (42፥16-17 ይመ)።

5፥27 *ተቀበለውም፤* የኤልፋዝ የመጨረሻ አስተያየት፣ ኢዮብ ከነኀጢአተኛነቱ (4፥7) እና እግዚአብሔርን ከመጥላት (ቍ 2) ራሱን ዝቅ ወደ ማድረግ (ቍ 11) እና ጽድቅን ወደ ተሞላው የእግዚአብሔር ቅጣት እንዲመለስ ነው (ቍ 17)፤ የኤልፋዝ ዐላማ ኢዮብን ማጽናናት ቢሆንም፣ በሐሰት ላይ የተመሠረቱ ክሶችን እያቀረበ ያቈስለዋል (2፥11)።

*6፥2-3፤* ኢዮብ በም 3 ላይ ያደረገውን ጠንካራ ንግግር በርኅራኄ እንዲረዱለት ያቀረበው ልመና (መግቢያኛ) ነው።

6፥4 *ሁሉን የሚችል አምላክ ፍላጻ፤* እንደ ኤልፋዝ ሁሉ ኢዮብም እግዚአብሔር እርሱን ለመቅጣት የፍርድ ቀስቱን የላከበት መሰለው፤ ሆኖም ይህ ቅጣት ለምን እንደደረሰበት አላወቀም (7፥20፤ 16፥12-13፤ ማሕ 3፥12 ይመ፤ ከዘጸ 32፥23፤ ከመዝ 7፥13፤ 38፥2 ጋር ያነጻጽሩ)።

*6፥5-6፤* ኢዮብ ከላይ ከባድ ሥቃይ ስለወረደበት፣ ከወዳጆቹም በመራራ ቃል ስላቈሰሉት እዬዬ ማለት ሲያንሰው ነው።

*6፥8-9፤* ኢዮብ በም 3 የተናገረውን ሐሳብ እዚህም ላይ ይደግመዋል።

*6፥10፤* ኢዮብ በዚህ ዓለም ለእግዚአብሔር ታማኝ ሆኖ መቈየቱን በወዲያኛው ዓለም እንደሚያውቅና በሐሤት እንደሚሞላ ይናገራል።

*6፥11-13፤* ኢዮብ አለኝ የሚለው አንዳች ነገር ባለ መኖሩ፣ ምንም ተስፋ እንደሌለው አድርጎ ራሱን ይቈጥራል።

6፥11 *እታገሥስ ዘንድ፤* የ9፥2-3 ማብ ይመ።

[14]"ለወዳጁ በጎነት የማያሳይ ሰው፣
ሁሉን የሚችለውን አምላክ መፍራት
ትቶአል::
[15]ወንድሞቼ ግን እንደማያዛልቅ ጅረት፣
ለጊዜው ሞልቶ እንደሚፈስ ወንዝ
የማይታመኑ ናቸው፤
[16]በረዶ በሟሟ ጊዜ ወንዙ ይደፈርሳል፤
ዐመዳይም በቀለጠ ጊዜ ይሞላል፤
[17]በበጋ ወራት ግን ይጠፋል፤
በሙቀትም ጊዜ መፋሰሻው ላይ
አይገኝም::
[18]ሲራራ ነጋዴዎች ውሃ አጥተው
መንገዳቸውን ይቀይራሉ፤
ወደ በረሓም ገብተው ይጠፋሉ::
[19]የቴማን ነጋዴዎች ውሃ ይፈልጋሉ
የሳባ መንገደኞችም ተስፋ ያደርጋሉ፤
[20]እርግጠኞች ሆነው ስለ ነበር ተስቀቁ፤
እዚያ ደረሱ፣ ግን ዐፈሩ::
[21]አሁንም እናንተ እንደዚያ ሆናችሁብኝ፣
መከራዬን አይታችሁ ፈራችሁ::
[22]ለመሆኑ፣ 'ስለ እኔ ሆናችሁ አንድ ነገር
ስጡልኝ፣
በዕዳ የተያዝብኝንም በሀብታችሁ
አስለቅቁልኝ!' ብያለሁን?
[23]ወይስ፤ 'ከጠላት አስጥሉኝ፤
ከጨካኝም እጅ ተቤዡኝ' አልኋችሁን?

[24]"አስተምሩኝ፤ እኔም ዝም እላለሁ፤
ምኑ ላይ እንደ ተሳሳትሁ ጠቍሙኝ::
[25]የቅንነት ቃል ምንኛ ኀያል ነው!
የእናንተ ክርክር ግን ምን ፋይዳ አለው?
[26]የተናገርሁትን ለማረም፣
ተስፋ የቈረጠውንም ሰው ቃል እንደ
ነፋስ ለመቍጠር ታስባላችሁን?
[27]በድኻ አደጉ ላይ ዕጣ ትጣጣላላችሁን?
ወይስ ወዳጃችሁን ትሸጣላችሁን?

[28]"አሁን ግን ፈቃዳችሁ ቢሆን ወደ እኔ
ተመልከቱ፤
ፊት ለፊት እዋሻችኋለሁን?
[29]መለስ በሉ፤ ፍርደ ገምድል አትሁኑ፤
ጽድቄ ጸንታ ቆማለችና መለስ ብላችሁ
አስተውሉ::

6፥14 ዘፍ17፥1፤ 1ሳሙ20፥42፤ኢዮ4፥5፤12፥4፤15፥4፤17፥2፡6፤19፥19፡21፤21፥3፤30፥1፡10፤መዝ38፥11፤69፥20፤1ዮሐ3፥17
6፥15 ኢዮ13፥4፤16፥2፤21፥34፤መዝ22፥1፤38፥11፤ኤር15፥18
6፥16 መዝ147፥18
6፥17 ኢዮ24፥19
6፥19 ዘፍ10፥7፡28፤25፥15
6፥20 ኤር14፥3፤ኢዩ1፥11
6፥21 መዝ38፥11
6፥22 ዘኍ35፥31፤ኢዮ33፥24፤መዝ49፥7፤ኤር15፥10
6፥23 2ነገ19፥19
6፥24 ኢዮ2፥10፤19፥ 4፤33፥33፤መዝ39፥1፤141፥3፤ምሳ10፥19፤11፥12፤17፥27፤መክ5፥2
6፥25 ኢሳ22፥23፤መክ12፥11
6፥26 ቍ3፤ዘፍ41፥6፤ኢዮ8፥2፤15፥3፤16፥3፤ኤር5፥13
6፥27 ዘፀ22፥22፡24፤ኢዮ31፥17፡21፤ኢሳ10፥2፤ሕዝ24፥6፤ኢዩ3፥3፤አብ1፥11፤ናሆ3፥10
6፥28 ኢዮ9፥15፤24፥25፤27፥4፤32፥10፥33፥1፡3፤34፥6፥36፥3፡4
6፥29 ኢዮ2፥3፤9፥21፤10፥7፤11፥2፤12፥4፤19፥6፤23፥7፡10፤27፥2፤33፥9፡32፤34፥5፡36፤35፥2፤40፥8፤42፥6፤መዝ66፥10፤ኢሳ40፥27፤ዘካ13፥9
6፥30 ኢዮ12፥11፤27፥4
7፥1 ዘሌ25፥50፤ኢዮ5፥7፤14፥14፤ኢሳ40፥2
7፥2 ዘሌ19፥13፤ኢዮ14፥1፡6፤መክ2፥23
7፥3 ኢዮ16፥7፤መዝ6፥6፤42፥3፤56፥8፤መክ4፥1፤ኢሳ16፥9፤ኤር9፥1፤ሰቆ1፥2፡16

[30]ከፉት በአንደበቴ አለን?
አፌስ ተንኰልን መለየት አይችልምን?

# 7

"የሰው ሕይወት በምድር ላይ ብርቱ
ተጋድሎ አይደለምን?
ዘመኑስ እንደ ምንደኛ ዘመን
አይደለምን?
[2]የምሽትን ጥላ እንደሚመኝ አገልጋይ፣
ደመወዙንም እንደሚናፍቅ ምንደኛ፣
[3]እንዲሁ ከንቱ ወራት ታደሉኝ፣
የጕስቍልና ሌሊቶችም ተወሰኑልኝ::
[4]በተኛሁ ጊዜ 'መቼ ነግቶ እነሣለሁ?'
እላለሁ፤
ሌሊቱ ይረዝማል፤ እስኪነጋም
እገላበጣለሁ::
[5]አካሌ ቈስሉ ትልና ቅርፊት ለብሶአል፤
ቈዳዬ አፈክፍኮአል፤ ቍስሌም
አመርቅዞአል::

[6]"ዘመኔ ከሸማኔ መወርወሪያ ይልቅ
ይፈጥናል፤
ያለ ተስፋም ያልቃል::
[7]ሕይወቴ ትንፋሽ ያህል እንደ ሆነች
አስብ፤
ዐይኔም ከእንግዲህ ደስታን አያይም::
[8]አሁን የሚያየኝ ሰው ዐይን ከእንግዲህ
አያየኝም፤
ትፈልገኛለህ፤ እኔ ግን የለሁም::
[9]ደመና በኖ እንደሚጠፋ፣
ወደ መቃብር[+] የሚወርድም
አይመለስም::
[10]ወደ ቤቱ ዳግመኛ አይመለስም፤
ስፍራውም ከእንግዲህ አያውቀውም::

7፥4 ቍ13-14፤ዘዳ28፥67 7፥5 ዘዳ28፥35፤ኢዮ17፥14፤21፥26፤24፥20፤25፥6፤ኢሳ14፥11 7፥6 ኢዮ9፥25፤13፥15፤14፥19፤17፥11፡15፤19፥10፤መዝ37፥4፤39፥5፤52፥9፤ኢሳ38፥12 7፥7 ቍ16፤ዘፍ27፥46፤ኢዮ10፥20፤መዝ39፥4፡5፡11፤62፥9፤78፥39፤89፥47፤144፥4፤መክ7፥15፤ያዕ4፥14 7፥8 ኢዮ3፥13፤8፥18፤15፥29፤20፥7፡9፡21፤27፥17፤መዝ37፥36፤103፥16፤ኢሳ41፥12፤ዮሐ16፥16፤ሐሥ20፥25 7፥9 2ሳሙ12፥23፤ኢዮ3፥13፡25፤11፥8፤14፥13፤17፥16፤26፥6፤38፥17፤አሞ9፥2 7፥10 ቍ8፤ኢዮ18፥21፤21፥18፤27፥21፡23፤መዝ37፥10፤58፥9፤104፥35፤ኤር18፥17፤19፥8

[+]9 የዕብራይስጡ ሲኦል ይላል

*6፥14-15፤* ገላ 6፥1 ይመ:: ኢዮብ መንፈሳዊ ድጋፍ የሚያስፈልገው ሰው ነበር፤ ወዳጆቹ ግን ተስፋ የሚጣልባቸው ሆነው አልተገኙም::

6፥15 *ወንድሞቼ፤* ኢዮብ ወዳጆቹን፣ "ወንድሞቼ" በማለት ምን ያህል ጨካኞች እንደ ነበሩ አጕልቶ ይገልጻል::

6፥19 *የቴማን፤* የኢሳ 21፥14 ማብ ይመ:: *ሳባ፤* የ1፥15 ማብ ይመ::

*6፥22-23፤* ገንዘብ ከማያስወጣቸው ከወዳጅነታቸውና ከምክራቸው በስተቀር ኢዮብ ከእነርሱ የፈለገው ምንም ነገር አልነበረም::

6፥25 *የቅንነት ቃል፤* ኢዮብ እንዲህ የሚለው የራሱን ቃል ነው::

*6፥26* ነፋስ፤ 8፥2 ይመ::

*6፥27፤* የኢዮብ ወዳጆች ከአታላይነታቸውም በላይ የሚራራ ልብ የሌላቸው ጨካኞች መሆናቸውን በመግለጥ ይከሳቸዋል::

*6፥29፤* ኢዮብ ስሜቱን በመቈጣጠር ወዳጆቹ የሐሰት ክሳቸውን እንዲያቆሙ ይለምናቸዋል::

*7፥1-21፤* ኢዮብ ለኤልፋዝ ተገቢውን ምላሽ ከሰጠ በኋላ በዚህኛው ክፍል አቤቱታውን ለእግዚአብሔር ያቀርባል::

7፥1 *ብርቱ ተጋድሎ፤* 14፥14 ይመ:: ይህ አገላለጥ በዕብራይስጡ ፈታኝ የሆነውን የውትድርና አገልግሎት ያመለክታል፤ በኢሳ 40፥2 (የዚህኑ ማብ ይመ) ላይ በባቢሎናውያን ያካሄዱት ምርኮ የተገለጠውም በዚህ መልክ ነው::

*7፥2 የምሽትን ጥላ፤* የቀኑ ሥራ የሚያበቃበት ጊዜ ነው::

*7፥5፤* የ2፥7 ማብ ይመ::

7፥7 *ሕይወቴ ትንፋሽ ያህል እንደ ሆነች፤* የማያቋርጥ ሥቃይ ደርሶበት ስለነበር፣ ሕይወት ትርጕም አልባ ሆናበታለች፤ (ቍ 3፤ እንዲሁም መዝ 144፥3-4 ይመ):: በዚህ ጊዜ ፈውስ አገኛለሁ የሚል እምነት ስላልነበረው፣ ከሞት በቀር ከሥቃይ የሚገላገልበት ያለ አልመሰለውም::

7፥8 *ትፈልገኛለህ... የለሁም፤* ቍ 21 ይመ::

7፥9 *ወደ መቃብር የሚወርድም አይመለስም፤* በሰው አስተሳሰብ ላይ የተመሠረተ ነው እንጂ ሃይማኖታዊ አስተምህሮ አይደለም:: የሙታንን መኖሪያ መመለሻ የሌለው ምድር ይሉታል (የቍ 21 ማብ ይመ)::

[11]“ስለዚህ ከቶ ዝም አልልም፤
በመንፈሴ ጭንቀት እናገራለሁ፤
በነፍሴም ምሬት አጕረመርማለሁ::
[12]በላዬ ጠባቂ ታደርግ ዘንድ፣
እኔ ባሕር ነኝን ወይስ የባሕር አውሬ?
[13]አልጋዬ ያጽናናኛል፣
መኝታዬም ማጕረምረሜን ይቀንስልኛል
ባልሁ ጊዜ፣
[14]አንተ በሕልም ታስፈራራኛለህ፤
በራእይም ታስደነግጠኛለህ፤
[15]ስለዚህ እንዲህ ሆኖ ከመኖር፣
መታነቅና መሞትን እመርጣለሁ::
[16]ሕይወቴን እጸየፋለሁ፤ ዘላለም መኖር
አልፈልግም፣
ዘመኔ እንደ እስትንፋስ ነውና ተወኝ::

[17]“ከፍ ከፍ ታደርገው ዘንድ፣
ልብህንም ትጥልበት ዘንድ ሰው ምንድን
ነው?
[18]በየማለዳው ትመረምረዋለህ፤
በየጊዜውም ትፈትነዋለህ::
[19]ዐይንህን ከእኔ ላይ አታነሣምን?
ምራቄን እንኳ እስክውጥ ፋታ
አትሰጠኝምን?
[20]ሰውን የምትከታተል ሆይ፤
ኀጢአት ብሠራ፣ አንተን ምን
አደርግሃለሁ?
ለምን ዒላማህ አደረግኸኝ?
ለምንስ ሸክም ሆንሁብህ?[*]
[21]መተላለፌን ለምን ይቅር አትልም?
ኀጢአቴንስ ለምን አታስወግድልኝም?
ትቢያ ውስጥ የምጋደምበት ጊዜ ደርሶአል፤
ትፈልገኛለህ፤ እኔ ግን የለሁም::”

## በልዳዶስ

8 ሹሐዊውም በልዳዶስ እንዲህ ሲል መለሰ፤

[2]“እንዲህ ያለውን ነገር የምትናገረው፣
ቃልህም እንደ ብርቱ ነፋስ የሚሆነው
እስከ መቼ ነው?
[3]እግዚአብሔር ፍትሕን ያጣምማልን?
ሁሉን ቻይ አምላክስ ጽድቅን
ያጣምማልን?
[4]ልጆችህ በእርሱ ላይ ኀጢአት ሠርተው
ከሆነ፣
ለኀጢአታቸው ቅጣት አሳልፎ
ሰጥቶአቸዋል::
[5]ነገር ግን አንተ ወደ እግዚአብሔር
ብትመለከት፣
ሁሉን ቻይ አምላክን ብትማፀን፣
[6]ንጹሕና ቅን ብትሆን፣እርሱ ስለ አንተ
አሁኑኑ ይነሣል
ወደ ተገቢውም ስፍራህ ይመልስሃል::
[7]ጅማሬህ አነስተኛ ቢመስልም፣
ፍጻሜህ እጅግ ታላቅ ይሆናል::

[8]“የቀደመውን ትውልድ ጠይቅ፤
አባቶቻቸውም የደረሱበትን መርምረህ
አግኝ፤

7፥11 ቍ13፤1ሳሙ 1፥10፤ኢዮ6፥3፤9፥27፡35፤10፥1፤13፥13፤21፥4፤23፥2፤መዝ6፥3፤2 2፥2፤40፥9፤ኢሳ38፥15፡17
7፥12 ቍ20፤ዘፍ 1፥21፤ኢዮ38፥8-11፤ ኢሳ1፥14
7፥13 ቍ11
7፥14 ዘፍ41፥8፤ኢዮ 3፥26፤9፥34
7፥15 1ነገ19፥4፤ ኢዮ6፥9፤ዮና4፥3፤ ራእ9፥6
7፥16 ቍ7፡19፤1ነገ 19፥4፤ኢዮ3፥22፤9፥21፤10፥20፤መዝ 39፥13
7፥17 ኢዮ4፥19፤ 22፥2፤መዝ8፥4፤144፥3፤ዕብ2፥6
7፥18 ኢዮ14፥3፤ 23፥10፤መዝ17፥3፤ 26፥2፤66፥10፤73፥14 ፤139፥1-6፡23፤143፥2
7፥19 ቍ16፤ኢዮ 9፥18፤13፥26፤14፥6፤ 27፥2፤መዝ139፥7
7፥20 ቍ12፤ኢዮ 6፥4፤35፥6፤ኤር7፥19
7፥21 ቍ8፤ዘፍ3፥ 19፤ኢዮ3፥13፤9፥28፤ 10፥9፡14፤16፥6፤34፥ 15፤መዝ7፥5፤22፥15፤ 90፥3፤104፥29፤119፥ 120፤ኢሳ43፥25፤ ኤር31፥34፤ዕብ1፥3
8፥1 ዘፍ25፥2፤ኢዮ 18፥1፤25፥1
8፥2 2ዜና36፥16፤ኢ ዮ6፥26፤11፥2፤18፥2
8፥3 ዘፍ18፥25፤ኢዮ 4፥17፤34፥12፤ኢሳ 29፥15፤ኤር12፥1፤ ሮሜ3፥5

8፥4 ኢዮ1፥19 8፥5 ኢዮ5፥8፡27፤9፥15 8፥6 ኢዮ5፥15፡24፤22፥27፤33፥26፤34፥28፤ኢሳ58፥9፤65፥24 8፥7 ኢዮ1፥10፡21፥13፤22፥21፤36፥11፤መዝ25፥13፤ኤር29፥11፤31፥17 8፥8 ዘዳ32፥7፤ መዝ71፥18

[*]20 ጥቂት የማሶሬቲክ ጽሑፍ ቅጆች፣ የጥንት የዕብራውያን ጸሐፍት ትውፊትና ሰብዓ ሊቃናት እንዲሁ ሲሆኑ አብዛኛው የማሶሬቲክ ጽሑፍ ቅጆች ግን *ለራሴ ሸክም ሆንሁ* ይላሉ::

7፥11 *ዝም አልልም፤* ኢዮብ፣ እርሱን እየተከታተለ እንዲያርፍ ያልተወው በመሰለው በእግዚአብሔር ላይ፣ “ፍትሕ አዛብ ተሀብኛል” ብሎ ሊጮኽ ቈርጦአል (ቍ 17-20):: *በመንፈሴ ጭንቀት እናገራለሁ፤* ኤር 4፥19 ይመ:: *በነፍሴም ምሬት፤* 10፥1፤21፥25፤27፥2 ይመ::

7፥12 *እኔ ባሕር ነኝን ወይስ የባሕር አውሬ?* 3፥8 እና ለአማራጭ የቀረበውን ማብ ይመ:: የሚጮኸው የባሕር አውሬ የሁከት ምሳሌ ነው (መዝ 74፥13-14 እና ማብ ይመ፤ ኢሳ 27፥1፤ 51፥9)፤ ኢዮብም እንደ አውሬው ተደርጎ እንዳይታይ ይቃወማል::

*7፥13-14፤* የሰላም እንቅልፍ በሚፈልግበት ጊዜ፣ ዕረፍት የነሣው የሌሊት ቅዠት፣ ከእግዚአብሔር የተላከ መሰለው::

7፥16 *ሕይወቴን እጸየፋለሁ፤* የ9፥21 ማብ ይመ::

7፥17 *ከፍ ከፍ ታደርገው ዘንድ... ሰው ምንድን ነው?* መዝ 144፥3 ይመ፤ ዓለምን እንዲገዛ ሰው በእግዚአብሔር አምሳል የተፈጠረ መሆኑን (ዘፍ 1፥27-28)፣ ከሚያመለክተው ከመዝ 8፥4-8 ጋር ያነጻጽሩ፤ የኢዮብ ቃል አቀማመጥ ከዚህ ጋር ተመሳሳይነት ያለው ይምሰል እንጂ፣ ዋናው ሐሳብ ግን ከዚህ ይለያል፤ ይኸውም እግዚአብሔር ሰውን ይመረምራል፤ ሲመረምረው ከመሥመሩ ተዛንፎ ካገኘው ግን፣ ያለርኅራኄ በቅጽበት መቅጣት የጌታ ዐላማ መሰለው::

7፥19 *ምራቄን እንኳ እስክውጥ፤* በቀሙ ለጥቂት ጊዜ እንኳ ፋታ አትሰጠኝም ማለት ነው::

7፥20 *ኀጢአት ብሠራ አንተን ምን አደርግሃለሁ?* ፍጹም እንዳልሆንሁ ዐውቃለሁ፤ ይሁን እንጂ ለዚህ ሁሉ ሥቃይ የሚያበቃኝ ምን በደል ፈጽሜአለሁ? ማለት ነው:: *የምትከታተል፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ በኢሳ 27፥3 ላይ የእግዚአብሔርን ርኅራኄ ለመግለጽ ገብቶአል፤ እዚህ ላይ ግን ኢዮብ ቃሉን የሚጠቀምበት በተቃራኒው ነው:: *ዒላማህ አደረግኸኝ፤* የ6፥4 ማብ ይመ:: *ሸክም ሆንሁብህ?* አንዳንድ የጥናት ቅጆች “በራሴ ላይ ሸክም ሆንሁኝ?” ይላሉ:: የጥንት የዕብራይስጥ ጸሐፍት “ለአንተ” የሚለው “በራሴ ላይ” ወደሚለው እንደ ተለወጠ ይገልጻሉ፤ ምክንያቱም “ለአንተ” በሚለው የዕብራይስጥ አገላለጽ ውስጥ የድፍረት ሐሳብ ስላለበት ነው::

7፥21 *መተላለፌን... ኀጢአቴንስ፤* ኢዮብ ኀጢአተኛ መሆኑን ይናዘዛል፤ ነገር ግን እግዚአብሔር ለምን ይቅር እንዳላለው አልተረዳም:: *ትቢያ ውስጥ የምጋደምበት፤* የመስጴጦምያውያን አባባል ሲሆን፣ የሟቹን የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ ይገልጣሉ::

8፥2 *እስከ መቼ... ?* 18፥1 ይመ:: በልዳዶስ ከኤልፋዝ ጋር ሲነጻጸር ትዕግሥት የሌለው ሰው መስሎ ይታያል::

8፥3 *እግዚአብሔር ፍትሕን ያጣምማልን?* ኢዮብ ፍትሕ አልተደረገም በማለት እስካሁን የተቃውሞ ድምፅ በይፋ አሳስማም::

*8፥5-6፤* በልዳዶስ የሚያቀርባቸው ምክንያቶች የሚከተሉት ናቸው፤ እግዚአብሔር ጻድቅ ፈራጅ ስለሆነ ኢዮብና ቤተ ሰቡ የሚሠቃዩት በኀጢአት ምክንያት ነው:: ኢዮብ ምሕረት እንዲደረግለት መጠየቅ አለበት፤ መንገዱን አስተካክሎ የሚጓዝ ከሆነም፣ እግዚአብሔር ያጣውን ሁሉ ይመልስለታል::

8፥6 *ንጹሕና ቅን ብትሆን፤* ኢዮብ በዚያ ሁኔታ ውስጥ እንዲያልፍ እግዚአብሔር ለምን እንደ ፈለገ እናውቃለን (1፥8፤ 2፥3 ይመ)፤ በልዳዶስ ግን ኢዮብ ግብዝና አስመሳይ ነው ሲል በእርግጠኝነት ይናገራል (ቍ 13 ይመ)::

*8፥7፤* ቍ 21 ይመ:: እዚህ ላይ በልዳዶስ ራሱ ከሚገነዘበው በላይ እውነት ተናገረ (42፥10-17 ይመ)::

8፥8 *የቀደመውን ትውልድ ጠይቅ፤* ኤልፋዝ የመናፍስትን ዓለም በመማጠን እውነት ትገኝ ዘንድ አሳሰበ (4፥12-21 ይመ)፣ በልዳዶስ ግን ሲወርድ ሲዋረድ ተከማችቶ በሚገኘው የዕውቀት ሀብት አማካይነት እውነት ትገኝ ዘንድ አመለከተ::

[9]እኛ ትናንት ስለ ተወለድን አንዳች
 አናውቅምና፤
 ዘመናችንም በምድር ላይ እንደ ጥላ
 ነው።
[10]እነርሱ የሚያስተምሩህና የሚነግሩህ፣
 ከልቦናቸውም ቃልን የሚያወጡ
 አይደሉምን?
[11]ደንገል ረግረግ በሌለበት ስፍራ
 ይበቅላልን?
 ቄጠማስ ውሃ በሌለበት ይለመልማልን?
[12]ገና በማደግ ላይ እያለ ሳይታጨድ፣
 ከሌሎች ዕፀዋት ፈጥኖ ይደርቃል።
[13]እግዚአብሔርን የሚረሱ መጨረሻቸው
 እንዲህ ነው፤
 አምላክ የለሽ ኑሮ የሚኖሩም ሁሉ
 ተስፋቸው ትጠፋለች።
[14]መተማመኛው ቀጭን ክር፣[a]
 ድጋፉም የሸረሪት ድር ነው።
[15]ድሩ ላይ ቢደገፍ፣ ይበጠስበታል፤
 አጥብቆም ቢይዘው አይደጸናም።
[16]ውሃ እንደ ጠገበ ተክል፣ ፀሓይ
 እየሞቀው፣
 ቅርንጫፉን ሁሉ በአትክልቱ ስፍራ
 ላይ ይዘረጋል።
[17]ሥሩን በድንጋይ ክምር ላይ
 ይጠመጥማል፤
 በዐለትም መካከል ስፍራ ያበጃል።
[18]ከስፍራው ሲወገድ ግን፣
 ያ ቦታ 'አይቼህ አላውቅም' ብሎ
 ይክደዋል።
[19]እነሆ፤ ሕይወቱ በዚህ ያከትማል፤[b]
 ሌሎች አትክልትም ከመሬት ይበቅላሉ።
[20]"እነሆ፤ እግዚአብሔር እንከን የሌለበትን
 ሰው አይጥልም፤
 የክፉዎችንም እጅ አያበረታም፤
[21]እንደ ገና አፍህን በሣቅ፤
 ከንፈሮችህንም በእልልታ ይሞላል።
[22]ጠላቶችህ ኀፍረት ይለብሳሉ፤
 የክፉዎችም ድንኳን ይጠፋል።"

8፥9 ዘፍ47፥9፤ 1ዜና29፥15፤2ዜና10፥6፤መዝ39፥6
8፥10 ምሳ1፥8፤2፥1-2፤4፥1
8፥11 ዘፀ2፥3፤ኢዮ40፥21፤ኢሳ19፥6፤35፥7
8፥12 ቊ19፤2ነገ19፥26፤ኢዮ18፥16፤20፥5፤መዝ90፥5-6፤102፥11፤ኢሳ34፥4፤40፥7:24
8፥13 ኢዮ6፥9፤11፥20፤13፥16፤15፥34፤20፥5፤27፥8፤34፥30፤መዝ9፥17፤37፥1-2:38፤50፥22፤73፥17፤112፥10፤ምሳ10፥28፤11፥7፤ኢሳ51፥13፤ኤር15፥9፤17፥6
8፥14 ቊ15፤ኢዮ27፥18፤ኢሳ59፥5
8፥15 ቊ14፤መዝ49፥11፤ማቴ7፥26-27
8፥16 መዝ37፥35፤80፥11፤ ኢሳ 16፥8፤ ኤር 11፥16
8፥18 ኢዮ7፥8፤14፥20፤20፥9፤መዝ103፥16
8፥19 ቊ12፤ኢዮ15፥30፤መዝ119፥90፤መክ1፥4
8፥20 ዘፍ18፥25፤ኢዮ1፥1
8፥21 ዕዝ3፥13፤ኢዮ5፥22፤35፥10፤መዝ47፥5፤107፥22፤118፥15፤126፥2፤132፥16፤ኢሳ35፥6
8፥22 1ሳሙ8፥3፤ኢዮ4፥21፤18፥6:14:21፤21፥28፤27፥7:8:18፤34፥26፤36፥6፤38፥13፤መዝ6፥10፤35፥26፤44፥7፤52፥5፤53፥5፤71፥13፤86፥17፤109፥29፤132፥18፤ምሳ14፥11፤ሕዝ7፥27፤26፥16

## ኢዮብ

9 ኢዮብ እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"በእርግጥ ነገሩ እንዲህ እንደ ሆነ
 ዐውቃለሁ፤
 ነገር ግን ሥጋ ለባሽ በእግዚአብሔር ፊት
 እንዴት ጻድቅ ሊሆን ይችላል?
[3]ሰው ከእርሱ ጋር ለመከራከር ቢፈልግ፣
 ከሺህ ጥያቄ አንዱን እንኳ መመለስ
 አይችልም።
[4]ጥበቡ ጥልቅ፣ ኀይሉም ታላቅ ነውና፤
 እርሱን ተቃውሞ ያለ አንዳች ጒዳት
 የሄደ ማን ነው?
[5]ሳያውቁት፣ ተራሮችን ይነቅላቸዋል፤
 በቍጣውም ይገለብጣቸዋል።
[6]ምድርን ከስፍራዋ ያናውጣታል፤
 ምሰሶዎቿንም ያንቀጠቅጣል።
[7]ፀሓይን ያዝታል፤ አትወጣምም፤
 ከዋክብትንም በማኅተም ያሽጋል።
[8]እርሱ ብቻውን ሰማያትን ዘርግቶአል፤
 በባሕርም ማዕበል ላይ ይራመዳል።

9፥2 ኢዮ4፥17፤ሮሜ3፥20 9፥3 ቊ12:14:29:32፤ኢዮ10፥2፤12፥14፤13፥9:14፤22፥4፤23፥7:13፤37፥19፤40፥2:5፤መዝ44፥21፤ኢሳ14፥24 9፥4 ቊ19፤2ዜና13፥12፤ኢዮ5፥9:13፤11፥6፤12፥13:16፤23፥6፤24፥22፤26፥12፤28፥12:20:23፤30፥18፤38፥36፤መዝ51፥6፤93፥4፤95፥3፤ምሳ2፥6፤8፥14፤መክ2፥26፤ኢሳ40፥26፤63፥1፤ኤር50፥24፤ዳን2፥20፤4፥35 9፥5 መዝ18፥7፤46፥2-3፤ኢሳ13፥13፤ሚክ1፥4፤ማቴ17፥20 9፥6 ዘፀ19፥18፤2ሳሙ22፥8፤ኢዮ26፥14፤36፥29፤37፥4-5፤መዝ75፥3፤ኢሳ2፥21፤13፥13፤24፥18-20፤አሞ8፥8፤ዕን3፥4፤ዕብ12፥26 9፥7 ኢሳ13፥10፤34፥4፤ኤር4፥23:28፤ሕዝ32፥8፤ኢል2፥2:10:31፤3፥15፤ሶፎ1፥15፤ዘካ14፥6 9፥8 ዘፍ1፥1:8፤ኢዮ38፥16፤መዝ77፥19፤ምሳ8፥28፤ኢሳ48፥13፤ዕን3፥15፤ማቴ14፥25፤ማር6፥48፤ዮሐ6፥19

[a]14 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጒም አይታወቅም
[b]19 ወይም ያለው ደስታ ሁሉ

8፥9 *ዘመናችንም በምድር ላይ እንደ ጥላ ነው፤* በቅኔ መጻሕፍት ተዘውትሮ የሚነገር ዐቢይ ሐሳብ ነው (14፥2፤ 1ዜና 29፥15፤ መዝ 102፥11፤ 144፥4፤ ማሕ 6፥12፤ 8፥13 ይመ)።

*8፥11-19፤* ከአባቶች በተገኘው ልምድ መሠረት ለሕይወት መመሪያ የሚሆን የጥበብ ግጥም ነው። ይህም በቊ 10 ላይ የተ ጀመረ ሲሆን፣ በቊ 20-22 ላይ በኢዮብ ሕይወት ተግባራዊ ሆኖአል።

*8፥20፤* በልዳዶስ ኢዮብን ክፉ ሰው እንደ ሆነ አድርጎ የገለጠው በቀጥታ ነው፤ ኤልፋዝ ግን ሐሳቡ ከበልዳዶስ የተለየ ባይሆንም፣ ሐሳብ አገላለጹ ኢርቱዕ በሆነ መልክ ነው።

*8፥21፤* የቊ 7 ማብ ይመ።

*9፥2-3፤* ኢዮብ ኀጢአተኛ አይደለሁም አላለም፤ ሆኖም ቀኑን አፍርድ ችሎት በማቅረብ አሁን ላጋጠመው ከፍተኛ ሥቃይ የሚያበቃ በደል አለመፈጸሙን ለማረጋገጥ ይወዳል። ተስፋ ከመቍረጥ ደረጃ ላይ ደርሶ ሳለ በእግዚአብሔር ላይ ምሬት አሰምቶአል (16-20፡ 22-24፡ 29-35፤ 10፥1-7፡ 13-17 ይመ)፤ ያም ሆኖ ግን እግዚአብሔርን አልተወም፤ ሰይጣን እንደ ተመኘውም (1፥11፤ 2፥5 ይመ)፣ የዐመፃ ቃል አልተናገረም (10፥2፤ 8-12 ይመ)፤ ም 42 ኢዮብ በእምነቱ ጸንቶ መገኘቱን ያመለክታል፤ ም 9-10 ደግሞ ኢዮብ በእምነቱ ቢጸናም ማናቸውንም ነገር በትዕግሥት አለመቀበሉን ያሳያሉ (4፥2፤ 6፥11፤ 21፥4 ይመ)። ሲወርድ ሲዋረድ በነበረው ግንዛቤ መሠረት የኢዮብን ትዕግሥተኛነት ያመለክታል ተብሎ የታሰበውን፣ ነገር ግን ትዕግሥተኛነቱን ሳይሆን፣ ጽናቱን የሚያሳየውን ያዕ 5፥11 ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ።

9፥3 *ለመከራከር፤* ቊ 14 ይመ። የኢዮብ ንግግር በፍርድ ቤት ቋንቋ የተሞላ ነው፤ "መመለስ" (ቊ 3:15:32)፣ "እሟገት ዘንድ" (ቊ 14)፣ "—ተሟጋቼን—እጠይቃለሁ" (ቊ 15)፣ "ጠር ቼው" (ቊ 16:19)፣ "በደለኛ ያደርገኛል" (ቊ 20)፣ "የፈራጆቿን" (ቊ 24)፣ "በምን ላይ እንዳልተስማማን" (10፥2)፣ "ምስክ ሮች" (10፥17)። ኢዮብ ጻድቅ መሆኑን ቢናገርም እግዚአብሔር ታላቅ አምላክ በመሆኑ ከእርሱ ጋር መሟገት (ቊ 14) ዋጋ እንደሌለው ገብቶታል። የኢዮብ ጽድቅ ለኢዮብ አልጠቀመውም (ቊ 15)።

*9፥5-10፤* የእግዚአብሔርን ታላቅነት የሚገልጽ ድንቅ ዝማሬ ነው። ኢዮብ ግን የእግዚአብሔር ኀይል በቅንነትና በእውነት የተሞላ መሆኑን ስላላስተዋለ በዝማሬው አልተባረከም።

9፥6 *ምሰሶዎቿንም፤* 26፥11 ይመ። በመሠረት ላይ ቆማ ለች ተብላ በዘይቤያዊ አገላለጽ የቀረበችው መሬት (38፥6፤ 1ሳሙ 2፥8፤ መዝ 75፥3፤ 104፥5 ይመ)፣ በ26፥7 ላይ የገለጸው ተለውጠ ያለ ምንም ድጋፍ ተንጣላ እንደምትገኝ ተመልክቶአል።

9፥8 *ሰማያትን ዘርግቶአል፤* አንድም 1) ሰማያትን ይፈጥ ራል (ኢሳ 44፥24 ይመ) 2) ወይም አንድ ሰው ድንኳንን እንደ ሚዘረጋጋ (መዝ 104፥2)፣ ወጋገን ፍንትው ብሎ እንዲወጣ ያደ ርጋል ማለት ነው። *ማዕበል ላይ ይራመዳል፤* የከንዓናውያን ጽሑ ፍ አሼራ የተባለች ጣዖት አምላክ የባሕርን ማዕበል ጸጥ ለማድ ረግ በባሕር ላይ ትራመዳለች (ይህችው ጣዖት የባሕር አምላክ በመባልም ትታወቃለች)፤ ልክ እንደዚሁ ሁሉ እግዚአብሔር በነ ውጥ ላይ የሚገኘውን ባሕር ጸጥ በማድረግ፣ "በማዕበል ላይ ይራ መዳል" ተብሎአል።

[9]እርሱ የድብና የኦሪዮን፣
የፕልያዲስና የደቡብ ከዋክብት ፈጣሪ ነው፤
[10]የማይመረመሩ ድንቅ ነገሮችን፣
የማይቈጠሩ ታምራትንም ያደርጋል።
[11]እነሆ! በአጠገቤ ሲያልፍ አላየውም፤
በጐኔም ሲሄድ፣ ልገነዘበው አልችልም።
[12]ቢነጥቅ፣ ማን ይከለክለዋል?
"ምን መሥራትህ ነው?" የሚለውስ፣
ማን ነው?
[13]እግዚአብሔር ቍጣውን አይመልስም፤
ረዓብን የሚረዱ እንኳ ይሰግዱለታል።
[14]"ታዲያ፣ ከእርሱ ጋር እሟገት ዘንድ፣
ልከራከረውም ቃላት እመርጥ ዘንድ፣
እንዴት እችላለሁ?
[15]ጻድቅ ብሆንም እንኳ፣ ልመልስለት አልችልም፤
ዳኛዬን ምሕረት ከመለመን ሌላ ላደርግ የምችለው የለም።
[16]ጠርቼው "አቤት!" ቢለኝም፣
ያዳምጠኛል ብዬ አላምንም።
[17]በዐውሎ ነፋስ ይሰብረኛል፤
ቍስሌንም ያለ ምክንያት ያበዛል፤
[18]ምሬትን አጠገበኝ እንጂ፣
ለመተንፈስ እንኳ ፋታ አልሰጠኝም።
[19]የኀይል ነገር ከተነሣ፣ እርሱ ኀያል ነው!
የፍትሕም ነገር ከተነሣ፣ መጥሪያ
ሊሰጠው[ፕ] የሚችል ማን ነው?
[20]ንጹሕ ብሆን እንኳ፣ አንደበቴ ይፈርድብኛል፣
እንከን የለሽ እንኳ ብሆን፣ በደለኛ ያደርገኛል።
[21]"ያለ ነቀፋ ብሆንም እንኳ፣
ስለ ራሴ ግድ የለኝም፤
የገዛ ሕይወቴንም እንቃታለሁ።
[22]ሁሉም አንድ ነው፤
'እርሱ ጻድቁንና ኀጥኡን ያጠፋል'
የምለውም ለዚህ ነው።
[23]መዓት ወርዶ ድንገት ሰው ሲጨርስ፣
በንጹሓን መከራ ይሣለቃል።
[24]ምድር በክፉዎች እጅ ስትወድቅ፣
እርሱ የፈራጆቿን ዐይን ይሸፍናል፤
ታዲያ፣ ይህን ያደረገው እርሱ ካልሆነ
ማን ሊሆን ይችላል?
[25]"ዘመኔ ከሚሮጥ ሰው ይልቅ ይፈጥናል፣
አንዳችም ደስታ ሳያይ ያልፋል።
[26]ከደንገል እንደ ተሠራ ታንኳ፣
ለመንጠቅ ቍልቍል እንደሚበር ንስር ይፈጥናል።
[27]'ማጕረምረሜን እረሳለሁ፤
ገጽታዬን ቀይሬ ፈገግ እላለሁ' ብል፣
[28]ንጹሕ አድርገህ እንደማትቈጥረኝ ስለማውቅ፣
መከራዬን ሁሉ እፈራለሁ።
[29]በደለኛ መሆኔ ካልቀረ፣
ለምን በከንቱ እለፋለሁ?
[30]ሰውነቴን በሳሙና[ኦ] ብታጠብ፣
እጄንም በልዩ መታጠቢያ ባነጻ፣
[31]ልብሴ እንኳ እስኪጸየፈኝ ድረስ፣
በዐዘቅት ውስጥ ታሰጥመኛለህ።
[32]"መልስ እሰጠው ዘንድ፣ እሟገተውም ዘንድ፣
እርሱ እንደ እኔ ሰው አይደለም።
[33]በሁለታችን ላይ እጅ የሚጭን፣
በመካከላችንም የሚዳኝ ቢኖር፣

9፥9 ዘፍ1፥16፤ኢዮ32፥22፤40፥15:19 9፥10 ዘዳ6፥22፤ኢዮ5፥9፤መዝ72፥18፤136፥4፤ኤር32፥20 9፥11 ኢዮ23፥8-9፤35፥14 9፥12 ቍ3፤ዘኍ23፥20፤ዘዳ32፥39፤ኢዮ11፥10፤ኢሳ14፥27፤29፥16፤43፥13፤45፥9፤ዳን2፥21፤4፥32፤ሮሜ9፥20 9፥13 ዘኍ14፥18፤ኢዮ10፥15፤26፥12፤መዝ78፥38፤87፥4፤89፥10፤ኢሳ3፥11፤6፥5፤30፥7፤48፥9፤51፥9 9፥14 ቍ3 9፥15 ቍ20:29፤ዘፍ18፥25፤1ሳሙ24፥12፤ኢዮ8፥5፤10፥15፤13፥19፤15፥6፤23፥4፤34፥5-6፤40፥2:5፤42፥7፤መዝ50፥6፤96፥13 9፥16 ኢዮ13፥22፤ሮሜ9፥20-21 9፥17 ኢዮ2፥3፤16፥12:14፤30፥16:22፤መዝ10፥10፤83፥15፤ኢሳ38፥13፤ዮና1፥4 9፥18 ኢዮ7፥19፤10፥1 9፥19 ቍ4፥33፤ነሀ9፥32፤ኤር49፥19 9፥20 ቍ15 9፥21 ቍ14፤ዘፍ6፥9፤ዘኍ11፥15፤ኢዮ6፥29፤7፥16፤10፥1፤13፥13፤34፥6:7 9፥22 ኢዮ3፥19፤10፥8፤መክ9፥2:3፤ሕዝ21፥3 9፥23 ኢዮ24፥1:12፤መዝ64፥4፤ዕን1፥3፤ዕብ11፥36፤1ጴጥ1፥7 9፥24 ኢዮ1፥15:17፤13፥14፤10፥3፤12፥6:9፤13፥1፤16፥11፤19፥7፤21፥7:16፤22፥18፤24፥12:23፤27፥2፤31፥35፤35፥15፤40፥8፤መዝ73፥3:12፤መክ8፥11፤ኢሳ41፥20፤ኤር12፥1፤ሰቆ3፥9 9፥25 ኢዮ7፥6:7፤10፥20 9፥26 ኢዮ24፥18፤39፥29፤መዝ46፥3፤ኢሳ18፥2፤ዕን1፥8 9፥27 ኢዮ7፥11 9፥28 ዘፀ34፥7፤ኢዮ3፥25፤7፥21 9፥29 ቍ3:15፤መዝ37፥33 9፥30 ኢዮ14፥4:17፤17፥9፤31፥7፤33፥9፤ኢሳ1፥15:18፤ኤር2፥22፤ሆሴ13፥12፤ሚል3፥2 9፥31 ኢዮ 7፥20፤34፥9፤35፥3፤መዝ35፥7፤40፥2፤51፥9፤73፥13፤ኤር2፥22፤ናሆ3፥6፤ሚል2፥3 9፥32 ቍ3፤ዘኍ23፥19፤መዝ143፥2፤መክ6፥10፤ሮሜ 9፥20 9፥33 ቍ19፤1ሳሙ2፥25

[ፕ]19 ሰብዓ ሊቃናት ይመልከቱ፤ የዕብራይስጡ ሊሰጠኝ ይላል
[ኦ]30 ወይም በረዶ

9፥9 *የድብና የኦሪዮን፣ የፕልያዲስና፤* እነዚህን ሦስቱን የከዋክብት ስብስቦች በ38፥31-32 እንደ ገና እናገኛቸዋለን፤ የመጨረሻዎቹ ሁለት የከዋክብት ስብስቦች ደግሞ በአሞ 5፥8 (ማብ ይመ) ላይ ይኛሉ። የጥንት እስራኤላውያን ስለ ጠፈር የነበራቸው ዕውቀት ውስን ቢሆንም፣ እግዚአብሔር እንደ ፈጠራቸው ስለ ሚያውቁ እርሱን ስለ ከዋክብት ከፍተኛ አድናቆት ነበራቸው።

*9፥10፤* ኤልፋዝም በ5፥9 ልክ እንደዚሁ ተናግሮአል።

9፥12 *ማን ይከለክለዋል?* እግዚአብሔር የወደደውን ለማድረግ የማይናወጥና ሉዓላዊ የሆነ መብት ያለው መሆኑን ለማስገንዘብ ኢዮብ በጥብቅ ይከራከራል።

9፥13 *ረዓብን፤* በኢያሱ ም 2 ላይ የተጠቀሰችው ጋለሞታዋ ረዓብ ሳትሆን፣ በትውፊት መሠረት የባሕር አውሬ ነው (26፥12 ይመ)፤ በሌላም ስፍራ ግብፅን ለማመልከት ገብቶአል (ኢሳ 30፥7 እና ማብ ይመ)፤ 3፥8፤ 7፥12 እና ማብ ይመ።

9፥15 *ዳኛዬን፤* የእግዚአብሔርን ሚዛናዊነት ማንም ማዛነፍ አይችልም፤ (ዘፍ 18፥25 እና ማብ ይመ)።

*9፥17፤* እግዚአብሔር ሰይጣንን ወደ ኢዮብ ሲልክ ታላቅ ዐላማ እንደነበረው ኢዮብ አላወቀም።

9፥20 *አንደበቴ ይፈርድብኛል፤* 15፥6 ይመ።

9፥21 *የገዛ ሕይወቴንም እንቃታለሁ፤* 7፥16 ይመ። ተስፋ መቍረጥ የሞላበት ንግግር ነው፤ ይህም በመጽሐፉ መጨረሻ ኢዮብ ንስሓ ሲገባ በከፊል ተደግሞአል (42፥6 ይመ)።

*9፥22-24፤* እግዚአብሔር ለኢዮብ ታላቅ ምስጢር ሆኖበታል፤ በኢዮብ አእምሮ ውስጥ ካልሆነ በቀር፣ ኢዮብ ለመግለጽ የሚሞክረው አምላክ ከዚህ ይገኛል የሚባል ዐይነት አይደለም፤ በመጽሐፍ ቅዱስ ራሱን የገለጸው አምላክ ሥነ ምግባራዊ ለሆነው ነገር ሁሉ ግድ አለው (በ38፥2 ላይ የተመለከተውን የእግዚአብሔርን ቃል በ40፥3 ላይ ከተመለከተው ከኢዮብ መልስ ጋር ያነጻጽሩ)።

9፥24 *የፈራጆቿን ዐይን ይሸፍናል፤* ኢዮብ፣ ዳኞች ወንጀልንም፣ ወንጀል አልባነትንም በትክክል እንዳያዩ ዐይኖቻቸውን ሸፍኖአቸዋል ሲል እግዚአብሔርን ይከስዋል።

9፥26 *ከደንገል እንደ ተሠራ ታንኳ፤* የዘዳ 2፥3 ማብ ይመ።

9፥28 *ንጹሕ አድርገህ እንደማትቈጥረኝ፤* ኢዮብ ኀጢአት የሌለበት ጻድቅ ሰው ተብሎ አይሁን እንጂ፣ በደል የማይገኝበት ሰው ተብሎ በእግዚአብሔር ፊት መቆም ይፈልጋል፤ ይኸውም ከደረሰበት ሥቃዩ ጋር የሚመጣጠን በደል እንዳልፈጸመ ይታወቅለት ዘንድ ነው።

9፥29 *በደለኛ መሆኔ ካልቀረ፤* እርሱ የተቀበለው አሳዛኝ ሥቃይ እንደሚያመለክተው ማለት ነው።

9፥33 *በመካከላችንም የሚዳኝ፤* የ5፥1 ማብ ይመ። እግዚአብሔር ኀያል በመሆኑ ኢዮብ ዐቅመቢስነት ተሰማው፤ ስለዚህ ጕዳዩን ወደ ፍርድ ችሎት ይዞ የሚቀርብለት ጠበቃ ፈለገ። ከዚህ ላይ ኢዮብ ስለ ጌታ ኢየሱስ መካከለኛነት መተንበዩ አይደለም፤ ኢዮብ የፈለገው ኀጢአቱን ይቅር የሚለውን ሳይሆን፣ በደለኛ አለመሆኑን የሚያረጋግጥለትን ጠበቃ ነውና (16፥20-21፤ 19፥25-26 ይመ)።

[34]ግርማው እንዳያስፈራኝ፣
ስንዚአብሔር በትሩን ከእኔ ላይ ቢያነሣ፣
[35]ሳልፈራው በተናገርሁት ነበር፤
አሁን ባለሁበት ሁኔታ ግን፣ አልችልም።

# 10

"ሕይወቴን እጅግ ጠላሁ፤
ስለዚህም ማጒረምረሜን ያለ ገደብ እለቃለሁ፤
በነፍሴም ምሬት እናገራለሁ።
[2]ስንዚአብሔርን እንዲህ እለዋለሁ፤
በምን ላይ እንዳልተስማማን ንገረኝ
እንጂ አትፍረድብኝ።
[3]የክፉዎችን ዕቅድ በደስታ እየተቀበልህ፣
እኔን ግን ስታስጨንቀኝ፣
የእጅህንም ሥራ ስታዋርድ ደስ ይልሃልን?
[4]አንተ ዐይንህ የሥጋ ለባሽ ዐይን ነውን?
ሟች የሆነ የሰው ልጅ እንደሚያይ
ታያለህን?
[5]ዘመንህ እንደ ሟች ሰው ዘመን ነውን?
ወይስ ዓመታትህ እንደ ሰው ዓመታት
ናቸውን?
[6]ታዲያ፣ በደሌን የምትፈላልግብኝ፣
ኀጢአቴንም የምትከታተለው ለምንድን
ነው?
[7]እኔ በደለኛ እንዳልሆንሁ፣
ከእጅህም ሊያስጥለኝ ማንም
እንደማይችል አንተ ታውቃለህ።

[8]"እጅህ አበጀችኝ፤ ሠራችኝም፤
መልሰህ ደግሞ ታጠፋኛለህን?
[9]እንደ ሸክላ እንዳበጀኸኝ አስብ፤
አሁን ደግሞ ወደ ትቢያ
ትመልሰኛለህን?
[10]እንደ ወተት አላፈሰስኸኝምን?
እንደ እርጎስ አላረጋኸኝምን?
[11]ቈዳና ሥጋ አለበስኸኝ፤
በዐጥንትና በጅማትም አገጣጥመህ
ሠራኸኝ።
[12]ሕይወትን ሰጠኸኝ፤ በጎነትንም አሳየኸኝ፤
እንክብካቤህም መንፈሴን ጠበቀ።

[13]"ይህን ሁሉ ግን በልብህ ሸሸግህ፣
ነገሩ በሐሳብህ እንደ ነበር ዐውቃለሁ፤
[14]ኀጢአትን ብሠራ ትመለከተኛለህ፤
መተላለፌንም ሳትቀጣ አታልፍም።
[15]በደለኛ ብሆን ወዮልኝ፤
ንጹሕ ብሆንም፣ ራሴን ቀና አላደርግም፤
ውርደትን ተከናንቤአለሁና፤
በመከራም ተዘፍቄአለሁ።[h]
[16]ራሴን ከፍ ከፍ ባደርግ፣ እንደ አንበሳ
ታደባብኛለህ፤
አስፈሪ ኀይልህን ደጋግመህ ታሳየኛለህ፤
[17]አዳዲስ ምስክሮችን ታመጣብኛለህ፤
ቍጣህንም በላዬ ትጨምራለህ፤
ሰራዊትህም ተከታትሎ ይመጣብኛል።

[18]"ታዲያ ለምን ከማሕፀን አወጣኸኝ?
ምነው ዐይን ሳያየኝ በሞትሁ ኖሮ!
[19]ምነው ባልተፈጠርሁ!
ወይም ከማሕፀን ቀጥታ ወደ መቃብር
በወረድሁ!
[20]ጥቂት የሆነው ዘመኔ እያለቀ አይደለምን?
ከሥቃዬ ፋታ እንዳገኝ ተወት አድርገኝ፤
[21]ወደማልመለስበት ስፍራ፣
ወደ ጨለማና ወደ ሞት ጥላ[i] አገር
ከመሄዴ በፊት፣
[22]ብርሃኑ እንደ ጨለማ ወደ ሆነበት፣
የሞት ጥላ ወዳረበበበት፣ ሥርዐት የለሽ
ወደ ሆነ ምድር፣
ድቅድቅ ጨለማ ወደ ሰፈነበት አገር
ሳልሄድ ተወኝ።"

## ሶፋር

# 11

ነዕማታዊው ሶፋር እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"ይህ ሁሉ ቃል መልስ ማግኘት
አይገባውምን?
ወይስ ተናጋሪ ሰው እንደ እውነተኛ
ይቈጠርን?

9፥34 ኢዮ6፥4፤7፥14፤21፤9፥33፤7፤መዝ32፥4፤39፥10፤73፥5 9፥35 ኢዮ7፥11፤15፥13፥21 10፥1 ዘኍ11፥15፤1ሳሙ1፥10፤1ነገ19፥4፤ኢዮ7፥11፤9፥18፥21 10፥2 ኢዮ9፥3፤13፥3፤40፥1፤ኢሳ3፥13፤ሆሴ4፥1፤5፥1፤12፥2፤ሚክ6፥2፤ሮሜ8፥33 10፥3 ቍ8፤ዘፍ1፥26፤ኢዮ4፥17፤9፥22፤24፤14፥15፤16፥9፥14፤19፥6፥21፤22፥10፤30፥13፥21፤31፥23፤34፥6፤19፤መዝ8፥6፤95፥6፤100፥3፤138፥8፤149፥2፤ኢሳ60፥21፤64፥8 10፥4 1ሳሙ16፥7፤ኢዮ11፥11፤14፥16፤24፥23፤28፥24፤31፥4፤34፥21፤41፥11፤መዝ11፥4፤33፥15፤119፥168፤139፥12፤ምሳ5፥21፤15፥3፤ኤር11፥20-23፤16፥17 10፥5 ኢዮ36፥26፤መዝ39፥5፤90፥2፥4፤102፥24፤2ጴጥ3፥8 10፥6 ኢዮ14፥16 10፥7 ቍ15፤ዘዳ32፥39፤ኢዮ6፥29፤11፥4፤16፥17፤27፥5፥6፤31፥6፤32፥1 10፥8 ቍ3፤ዘፍ2፥7፤2ሳሙ14፥14፤ኢዮ30፥15 10፥9 ዘፍ2፥7፤ኢዮ4፥19፤7፥21፤ኢሳ29፥16 10፥11 መዝ139፥13፥15 10፥12 ዘፍ2፥7፤24፥12፤45፥5፤1ጴጥ2፥25 10፥13 ኢዮ23፥13፤መዝ115፥3 10፥14 ዘፀ34፥7፤ኢዮ7፥21፤13፥27 10፥15 ቍ7፤ኢዮ9፥13፥15፤መዝ25፥16 10፥16 1ሳሙ17፥34፤ኢዮ5፥9፤መዝ7፥2፤ኢሳ28፥21፤29፥14፤38፥13፤65፥7፤ኤር5፥6፤25፥38፤ሰቆ3፥10፤ሆሴ5፥14፤13፥7 10፥17 ሩት1፥21፤1ነገ21፥10፤ኢዮ5፥7፤16፥8 10፥18 ኢዮ3፥8፥26፤መዝ22፥9፤መክ6፥12 10፥19 ኢዮ3፥3፤ኤር15፥10 10፥20 ኢዮ7፥7፥16፤9፥25፤14፥1፤መክ4፥2፤7፥1 10፥21 2ሳሙ12፥23፤ኢዮ3፥5፥13፤16፥22፤መዝ 39፥13፤መክ12፥5 10፥22 1ሳሙ2፥9፤ኢዮ3፥5፥13

[h]15 ወይም *መከራዬን ዐውቄአለሁ*
[i]21 ወይም *ከባድ ጥላ እንዲሁም ቍ 22*

*9፥34፤* 13፥21 ይመ። *እግዚአብሔር በትሩን፤* የመለኮታዊ ፍርድና ቅጣት ምልክት ነው (መዝ 89፥32፤ ሰቆ 3፥1 ይመ)።

10፥1 *ሕይወቴን እጅግ ጠላሁ፤* የ9፥21 ማብ ይመ። *በነፍሴም ምሬት፤* ኢዮብ ምሬት ውስጥ ስለ ገባ፣ አእምሮው ስለ ልዑል እግዚአብሔር ያውጠነጠነው ሐሳብ፣ ትክክለኛ ግንዛቤ የሚሰጥ አይደለም።

*10፥3፤* እግዚአብሔር በክፉዎች አካሄድ ደስ እንደሚሰኝ፣ በደል በሌለበት በእርሱ ላይ ግን (9፥28 እና ማብ ይመ) ቍጣውን ያወረደ መሆኑን በማሰብ ኢዮብ አጉል ስሜት ውስጥ ገባ። ታመው በተኙበት ቦታ ደርዝ ላለው ትምህርተ መለኮት የተመቸ አለመሆኑን የሚያሳይ ነው። ሰዎች በመራር ሥቃይ ላይ ሲገኙ ፍቅርና ሐዘኔታ ይደረግላቸው ዘንድ አስፈላጊ ነው። ኢዮብ የማታ ማታ ንስሓ ይገባል፤ እግዚአብሔርም እንደቸርነቱ ይቅርታ ያደርግለታል (42፥1-6)።

10፥4 *ዐይንህ የሥጋ፤* ፍጹም እንዳልሆነው እንደ ሰው ዕይታ ማለት ነው።

*10፥8-17፤* ኢዮብ እግዚአብሔርን እንደ ባላንጣው በመቍጠር አሁንም ጥያቄውን ያቀርባል። እግዚአብሔር ኢዮብን በእናቱ ማሕፀን ግሩምና ድንቅ አድርጎ ሠርቶት ሳለ፣ ሥቃይ ተቀባዩ ኢዮብም ያለበደል መሆኑ እየታወቀ፣ እግዚአብሔር ኢዮብን ለምን በሥቃይ ውስጥ እንዲሆን እንደ ፈለገ ኢዮብ ለማወቅ ይጠይቃል።

*10፥8-11፤* እግዚአብሔር ሕፃንን በማሕፀን ውስጥ መፍጠሩን የሚያሳይ ቅኔአዊ አገላለጽ ነው (መዝ 139፥13-16 ይመ)።

10፥9 *እንደ ሸክላ እንዳበጀኸኝ፤* የ4፥19 ማብ ይመ። *ወደ ትቢያ ትመልሰኛለህን?* የዘፍ 3፥19 ማብ ይመ።

*10፥15-16፤* በደለኛም ይሁን በደል አልባ፣ ሁሉን ቻይ እግዚአብሔር ለእርሱ እንደ ጽድቅ እንደማይፈርድለት ኢዮብ ያስባል።

10፥17 *ምስክሮችን ታመጣብኛለህ፤* የ9፥3 ማብ ይመ።

*10፥18-22፤* የም 3 ማብ ይመ።

10፥21 *ወደማልመለስበት ስፍራ፤* የ7፥9 ማብ ይመ። *ወደ ጨለማና ወደ ሞት ጥላ አገር፤* 38፥17 ይመ። ጥንታዊው የመስጴጦምያ ጽሑፍ መቃብርን "የጨለማ ቤት" ይለዋል።

*11፥1-20፤* እንደ ኤልፋዝና (4፥7-11 ይመ) እንደ በልዳዶስ (8፥3-6 ይመ) ሶፋርም ኢዮብን ለዚህ ሁሉ ሥቃይ የዳረገው ኀጢአቱ እንደ ሆነ ይናገራል።

*11፥2-3፤* ሶፋር የኢዮብ ሥቃይ ምን ያህል መሆኑን ሳይረዳ ማውገዙ፣ ርኅራኄ እንደሌለው ያመለክታል። በሌላም በኩል

[3]በውኑ የአንተ መዘላበድ ሰውን ዝም
ያሰኛልን?
ስታፌዝስ የሚገሥጽህ የለም?
[4]እግዚአብሔርንም፣ 'ትምህርቴ የጠራ፤
በዐይንህም ፊት የጸዳሁ ነኝ' ትለዋለህ::
[5]ምነው እግዚአብሔር ቢናገርህ!
ከንፈሩንም በአንተ ላይ ቢከፍት!
[6]እውነተኛ ጥበብ ባለ ብዙ ፈርጅ ናትና፣
የጥበብንም ምስጢር ምነው በገለጠልህ!
እግዚአብሔር ለኀጢአትህ የሚገባውን
እንዳላስከፈለህ ባወቅህ ነበር::

[7]"የእግዚአብሔርን ጥልቅ ምስጢር ልትለካ
ትችላለህን?
ወይስ ሁሉን የሚችለውን አምላክ
መርምረህ ትደርስበታለህን?
[8]ከሰማይ ይልቅ ከፍ ይላል፤ ምን ልታደርግ
ትችላለህ?
ከሲኦልም* ይጠልቃል፤ ምን ልታውቅ
ትችላለህ?
[9]መጠኑ ከምድር ይልቅ ይረዝማል፤
ከባሕርም ይልቅ ይሰፋል::

[10]"እርሱ ተከታትሎ መጥቶ በግዞት
ቢያስቀምጥህ፣
የፍርድ ሸንጎም ቢሰበስብ፣ ማን
ሊከለክለው ይችላል?
[11]በእውነት እርሱ ሸፍጠኞችን ያውቃል፣
ክፋት ሲሠራም ልብ ይላል::
[12]ጅል ሰው ጥበበኛ ከሚሆን ይልቅ፣
የሜዳ አህያ ሰው ሆኖ ቢወለድ
ይቀላል::[0]

[13]"ነገር ግን ልብህን ብትሰጠው፣
እጅህንም ወደ እርሱ ብትዘረጋ፣
[14]በእጅህ ያለውን ኀጢአት ብታርቅ፣
ክፋትም በድንኳንህ እንዳይኖር
ብታደርግ፣
[15]በዚያን ጊዜ ሳታፍር ቀና ትላለህ፤
ያለ ፍርሀት ጸንተህ ትቆማለህ፤
[16]መከራህን ትረሳለህ፤
ዐልፎ እንደ ሄደ ጐርፍም ታስበዋለህ::
[17]ሕይወትህ ከቀትር ይልቅ ያበራል፤
ጨለማውም እንደ ንጋት ይሆናል::
[18]ተስፋ ስላለ ተደላድለህ ትቀመጣለህ፤
ዙሪያህን ትመለከታለህ፤ በሰላምም
ታርፋለህ::
[19]ያለ አንዳች ሥጋት ትተኛለህ፤
ብዙ ሰዎችም ደጅ ይጠኑሃል::
[20]የክፉዎች ዐይን ግን ትጨልማለች
ማምለጫም አያገኙም፤
ተስፋቸውም ሞት ብቻ ነው::"

## ኢዮብ

## 12

ኢዮብ እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"በእርግጥ ሰው ማለት እናንተ
ናችኍ!
ጥበብም ከእናንተ ጋር ትሞታለች!
[3]ነገር ግን እኔም እንደ እናንተ አእምሮ
አለኝ፤
ከእናንተ አላንስም፤
እንዲህ ያለውን ነገር የማያውቅ ማን
ነው?

11፥1 ኢዮ2፥11
11፥2 ዘኍ41፥6፤ ኢዮ6፥29፤8፥2፤16፥3
11፥3 ኢዮ12፥4፤ 16፥10፤17፥2፤21፥3፤ 30፥1፤መዝ1፥1፤ኤፌ 4፥29፤5፥4
11፥4 ኢዮ9፥21፤ 10፥7
11፥5 ዘፀ20፥19፤ ኢዮ23፥5፤32፥13፤ 38፥1
11፥6 ዕዝ9፥13፤ ኢዮ9፥4፤15፥5፤ 1ቆሮ2፥10
11፥7 ኢዮ5፥9፤ምክ 3፥11
11፥8 ዘኍ15፥5፤ ኢዮ7፥9፤15፥13፡25፤ 22፥12፤25፥2፤33፥13 ፤40፥2፤መዝ57፥10፤ 139፥8፤ኢሳ55፥9፤ ኤፌ3፥18
11፥9 ኢዮ22፥12፤ 35፥5፤36፥26፤37፥5፡ 23፤ኢሳ40፥26፤ኤፌ 3፥19-20
11፥10 ኢዮ9፥12፤ ራእ3፥7
11፥11 ኢዮ10፥4፤ 31፥37፤34፥11፡25፤ 36፥7፤መዝ10፥14
11፥12 ዘኍ16፥12፤ 2ዜና6፥36
11፥13 ዘፀ9፥29፤ 1ሳሙ7፥3፤ኢዮ5፥8፡ 27፤መዝ78፥8
11፥14 ኢሱ24፥14፤ ኢ.22፥23፤መዝ101፥4
11፥15 ዘኍ4፥7፤ 1ሳሙ2፥9፤ኢዮ22፥ 26፤መዝ3፥6፤20፥8፤3 7፥23፤40፥2፤119፥5፤ ኤፌ6፥14
11፥16 ኢሱ7፥5፤ ኢዮ22፥11፤መዝ58፥ 7፤112፥10፤ኢሳ26፥ 16፤37፥3፤65፥16፤ ሕዝ21፥7
11፥17 ኢዮ17፥12፤18፥6፤22፥28፤29፥3፤መዝ18፥28፤37፥6፤112፥ 4፤119፥105፤ኢሳ5፥20፤58፥8፡10፤ 62፥1፤ዮሐ8፥12 11፥18 ዘሌ 26፥6፤መዝ3፥5፤4፥8፤127፥2፤ምሳ3፥24፤መክ5፥12፤ኢሳ11፥10፤14፥ 3፤28፥12፤30፥15፤ 32፥18፤ዘካ3፥10 11፥19 ዘሌ26፥6፤ኢሳ45፥14
11፥20 ዘዳ28፥65፤ኢዮ8፥13፤12፥10፤17፥5፤18፥18፤27፥22፤34፥ 22፤36፥6፤መዝ139፥11-12፤ኤር11፥11፤23፥24፤25፥35፤አሞ2፥14፤ 9፥2-3 12፥2 ኢዮ15፥8፤17፥10 12፥3 ኢዮ13፥2፤15፥9

*8 *ወይም ከመቃብር*
012 *ወይም የዱር አህያ ለማዳ ሆኖ ሊወለድ ይችላል*

ሶፋር ያን ያህል ውግዘት ማውረዱ ትክክል አይደለም፤ ኢዮብ በቅን ልቦና ተነሣሥቶ የእግዚአብሔር አሠራር የቱን ያህል ምስጢር እንደሆነበት ገልጸአል (9፥14-24 ይመ)፤ ይሁን እንጂ ሶፋር በከንቱ ሊከሰው ጸያፍ የሆነ ቃል በእግዚአብሔር ላይ አላሰ ማም::

11፥4 *የጸዳሁ ነኝ፤* በ10፥7፡15 ላይ ኢዮብ በደለኛ እንዳ ልሆነ ይናገራል፤ በ9፥21 ላይ ደግሞ እንከን የማይገኝበት መሆኑን ይናገራል፤ ይህም በ1፥8፤ 2፥3 ላይ እግዚአብሔር ስለ ኢዮብ ከሰጠው ምስክርነት ጋር ይመሳሰላል:: ሶፋር ግን ኀጢአት የሌ ለብኝ ፍጹም ሰው ነኝ ብሎ እንደ ተናገረ አድርጎ ኢዮብን ይከ ሳል፤ ኢዮብ ግን የትም ቦታ በእንዲህ ዐይነት አገላለጽ አልተጠ ቀመም::

*11፥5፤* ሶፋር፣ እግዚአብሔር በኢዮብ ላይ የቍጣ ቃል የሚናገር መስሎት ነበር፤ ነገር ግን እግዚአብሔር በመጨረሻ የቍጣ ቃል ያሰማው በሶፋር ላይ ነው (42፥7 ይመ)::

11፥6 *እውነተኛ ጥበብ ባለ ብዙ ፈርጅ ናትና፤* የብሉይ ኪዳን የቅኔ መጻሕፍት (በተለይም መጽሐፈ ምሳሌ) ሥውር ትር ጕም ያላቸውን ምሳሌዎችን፣ እንቆቅልሾችንና ተምሳሌቶችን በብ ዛት ተጠቅመዋል:: በሶፋር ግምት ኢዮብ ስለ እግዚአብሔር ያለው ዕውቀት ላይ ላዩን ነው፤ ማስተዋልም የለውም (ቍ 7-9 ይመ)::

*11፥7፤* ሶፋር በ38፥1-42፥6 ላይ ያለውን የጌታን ቃል፣ ወደፊት እንዲህ ሳይሆን አይቀርም ብሎ ያሰበው ካለማስተዋል የተነሣ ነው:: /

*11፥8-9፤* ሶፋር የእግዚአብሔርን ዕውቀት ጥልቀቱን፣ ከፍታውን፣ ስፋቱንና ርዝመቱን እንደሚገልጽ ሁሉ ጳውሎስም የክርስቶስን ፍቅር እንደዚሁ ይገልጻል (ኤፌ 3፥18 ይመ)::

11፥8 *ምን ልታደርግ ትችላለህ?* ወደ ሰማይ ወጥተህ የእግዚአብሔርን ዕውቀት መመርመር ትችላለህን?

11፥11-12 *ሸፍጠኞችን... ጅል ሰው፤* ኢዮብ በታምር ካልሆነ በቀር ከቶ እንደማይለወጥ ሶፋር ይናገራል::

*11፥13-20፤* ሶፋር የኢዮብ ችግር መንሥኤው ኀጢአቱ እንደ ሆነ ያስባል፤ ይህ ከሆነ ደግሞ ኢዮብ ማድረግ ያለበት ንስሓ መግባት ነው፤ ከዚያም ሕይወቱ የተባረከና አስደሳች ይሆናል:: እግዚአብሔር ግን እኛ ልጆቹ በመሆናችን ሕይወታ ችን፣ "ከቀትር ይልቅ" እንደሚበራ (ቍ 17) ቃል አልገባልንም:: ጌታ ለእኛ ለልጆቹ ከዚህ ዓለም ምቾት ወይም ሌሎች፣ "ደጅ ይጠኑሃል" (ቍ 19) ከሚለው የላቀ ዐላማ አለው:: የሶፋር ፍልስፍና ከመዝ 73 ጋር የሚጋጭ ነው::

11፥13 *እጅህንም ወደ እርሱ ብትዘረጋ፤* ለርዳታ ማለት ነው (ምሳ 1፥24፤ ሰቆ 1፥17 ይመ)::

11፥15 *ሳታፍር ቀና ትላለህ፤* ሶፋር በ10፥15 ላይ የተጠቀ ሰውን የኢዮብን ሐሳብ ላይ ያስተጋባል::

*11፥20፤* በልዳዶስም በተመሳሳይ መንገድ ንግግሩን ይደ መድማል (8፥22 ይመ)::

*12፥1-14፡22፤* ቀደም ሲል እንደነበረው አሁንም የኢዮብ መልስ ሁለት ክፍል አለው፤ ይህም ከሦስት ወዳጆቹ ጋር የሚያደርገው ውይይት (12፥2-13፥19) ከዚያም ለእግዚአብሔር የሚያቀርበው መልስ (13፥20-14፥22) ነው::

*12፥2፤* ኢዮብ ለመጀመሪያ ጊዜ መካሪዎቹን በምጸት ይናገራል (ቍ 20 ይመ)::

12፥3 *የማያውቅ ማን ነው?* ቍ 9 ይመ:: ወዳጆቹ ለኢ ዮብ የሰጡት ምክር ተራ ነገርና ዋጋ ቢስ ነው::

[4]እግዚአብሔርን ጠርቼ የመለሰልኝ ሰው
ብሆንም፣
ለባልንጀሮቼ መሣቂያ ሆኛለሁ፤
ጻድቅና ያለ ነቀፋ ሆኜ እያለሁ፣ መሣቂያ
ሆኛለሁ።
[5]የደላቸው በመከራ ያፌዛሉ፤
እግሩ የተንሸራተተውንም ይገፈትራሉ።
[6]የቀማኞች ድንኳን አይታወክም፤
አምላካቸውን በእጃቸው ይዘው እየዞሩም፣*
እግዚአብሔርንም እያስቈጡ በሰላም
ይኖራሉ።

[7]"እስቲ እንስሶችን ጠይቅ፤
ያስተምሯችኋል፤
የሰማይ ወፎችንም ጠይቅ፣
ይነግሯችኋል፤
[8]ለምድር ተናገሩ፤ ታስተምራችኋለች፤
የባሕርም ዓሣ ይነግራችኋል።
[9]የእግዚአብሔር እጅ ይህን እንዳደረገ፣
ከእነዚህ ሁሉ የማያውቅ ማን ነው?
[10]የፍጥረት ሁሉ ሕይወት፣
የሰውም ሁሉ መንፈስ በእጁ ናትና፤
[11]ምላስ የምግብን ጣዕም እንደሚለይ፣
ጆሮ ቃላትን አይለይምን?
[12]ጥበብ ያለው በአረጋውያን ዘንድ
አይደለምን?
ማስተዋልስ ረጅም ዕድሜ ባላቸው ዘንድ
አይገኝምን?

[13]"ጥበብና ኀይል የእግዚአብሔር ናቸው፤
ምክርና ማስተዋልም በእርሱ ዘንድ
ይገኛሉ።
[14]እርሱ ያፈረሰውን መልሶ የሚገነባ የለም፣
እርሱ ያሰረውን የሚፈታ አይገኝም።
[15]እርሱ ውሃን ቢከለክል፣ ድርቅ ይሆናል፤
ቢለቀውም ውሃው ምድሪቱን
ያጥለቀልቃል።
[16]ብርታትና ድል ማድረግ በእርሱ ዘንድ
ይገኛል፤
አታላዩም ተታላዩም በእርሱ እጅ
ናቸው።
[17]አማካሪዎችን ከተበባቸው ያራቍታል፤
ፈራጆችንም ማስተዋል ይነሣል።
[18]ነገሥታትን ድግ ያስፈታል፤
ገመድም በወገባቸው ያስራል።*
[19]ካህናትን ከክህነታቸው ያዋርዳል፤
ለዘመናት የተደላደሉትንም ይገለብጣል።
[20]ዕውቅ መካሪዎችን ቋንቋ ያሳጣል፤
የሽማግሌዎችንም ማስተዋል ይወስዳል።
[21]የተከበሩትን ውርደት ያከናንባል፤
ብርቱዎችንም ትጥቅ ያስፈታል።
[22]የጨለማን ጥልቅ ነገሮች ይገልጣል፤
የሞትንም ጥላ ወደ ብርሃን ያወጣል።
[23]ሕዝቦችን ታላቅ ያደርጋል፤ መልሶም
ያጠፋቸዋል፤
ሕዝቦችን ያበዛል፤ ያፈልሳቸዋልም።
[24]የዓለም መሪዎችን ማስተዋል ይነሣል፤
መንገድ በሌለበት በረሓም
ያቅበዘብዛቸዋል፤
[25]ብርሃን በሌለበት ጨለማ በዳበሳ ይሄዳሉ፤
እንደ ሰካራምም ይንገዳገዳሉ።

# 13

"ይህን ሁሉ ዐይኔ አይቶአል፤
ጆሮዬም ሰምቶ አስተውያለሁ፤
[2]እናንተ የምታውቁትን፣ እኔም
ዐውቃለሁ፤
ከእናንተ የማንስ አይደለሁም።
[3]ነገር ግን ሁሉን ከሚችል አምላክ ጋር

12፥4 ዘፍ6፥9፥38፥23፤ኢዮ6፥14፥29፥11፥31፥15፥16፥16፥10፤19፥14፤መዝ91፥15 12፥5 መዝ17፥5፤37፥31፥38፥16፥66፥9፥73፥2፥94፥18፤123፥4 12፥6 ኢዮ5፥24፤9፥24 12፥7 ኢዮ18፥3፤35፥11፤ማቴ6፥26፤ሮሜ1፥20 12፥9 ኢዮ9፥24፤ኢሳ1፥3 12፥10 ዘፍ2፥7፤ዘኍ16፥22፤ኢዮ11፥20፤ዳን5፥23፤ሐሥ17፥28 12፥11 ኢዮ34፥3 12፥12 ቍ20፤1ነገ4፥2፤ኢዮ15፥10፥17፥4፥32፥7፥9፥34፥4፥10 12፥13 ዘኍ23፥19፤1ነገ3፥12፤ኢዮ9፥4፤32፥8፥38፥36፤ምሳ2፥6፥21፥30፤ኢሳ40፥13-14፥45፥9፤ኤር32፥19፤ዳን1፥17፤1ቆሮ1፥24 12፥14 ዘጸ13፥16፤ኢዮ9፥3፥16፥9፥19፥10፤መዝ127፥1፤ኢሳ22፥22፥24፥20፥25፥2፤ሕዝ26፥14፤ራእ3፥7 12፥15 ዘፍ7፥24፤ዘዳ28፥22፤1ነገ17፥1፤ኢዮ28፥25፤ኢሳ40፥12 12፥16 2ዜና18፥22፤ኢዮ9፥4፥13፥7፥9፥27፥4፤ሮሜ2፥11 12፥17 ቍ19፤ኢዮ3፥14፥19፥9፤ኢሳ20፥4፤1ቆሮ1፥20 12፥18 ቍ21፤ኢዮ34፥18፤መዝ107፥14፥40፥116፥16፤ኢሳ5፥27፥40፥23፤ናሆ1፥13 12፥19 ቍ17፤ዘዳ24፥15፤ኢዮ9፥24፥14፥20፥22፥8፥24፥12፥22፥34፥20፥28፥35፥9፤ኢሳ2፥22፤31፥8፥40፥17፥23፤ኤር25፥18፤ዳን2፥21፥34፤ሉቃ1፥52 12፥20 ቍ12፥24፤ዳን4፥33፥34 12፥21 ቍ18፤ኢዮ3፥15፤ኢሳ34፥12 12፥22 ኢዮ3፥5፤መዝ139፥12፤ዳን2፥22፤1ቆሮ4፥5 12፥23 ዘፀ34፥24፤ኢዮ5፥12፤መዝ2፥1፥46፥6፥107፥38፤ኢሳ9፥3፥13፥4፥26፥15፤54፥3፤ኤር25፥9፤ሐሥ17፥26 12፥24 ቍ20፤መዝ107፥40 12፥25 ዘዳ28፥29፤ኢዮ18፥6፥21፥17፥29፥3፤መዝ107፥27፤ኢሳ24፥20

*6 ወይም የእግዚአብሔር እጅ በምታመጣቸው ነገር
*18 ወይም የነገሥታትን ድግ… ፤ ወቅ ያስራል

12፥4 *እግዚአብሔርን ጠርቼ የመለሰልኝ፤* የሥቃይ ዘመኑ ከመጀመሩ በፊት በነበረው ሕይወቱ ማለት ነው (ከ9፥16 ጋር ያነጻጽሩ)።

*12፥5፤* በምቾት ላይ ያሉ ሰዎች እንደ ኢዮብ መከራ ያገኛቸውን ሰዎች ይንቃሉ።

*12፥6፤* እንዲህ ዐይነቱ ሐሳብ (9፥21-24 ይመ) መካሪዎችን ያበሳጫል፤ ይህም ኢዮብን፣ "የተንገደገደ ሰው" (ቍ 5) የሚል ቅጥያ እንዲለጥፉበት አድርጎአቸዋል።

*12፥7-12፤* እግዚአብሔር የወደደውን እንደሚያደርግ፣ ሰው ከሥቃዩ ይድንም ዘንድ የግል እምነቱ ዋስትና እንደማይሰጠው ለማስረዳት በእስቲ ተመልከቱት መልክ ያቀረበው ማስረጃ የጠቅላላውን የተፈጥሮን ሁኔታ ነው።

12፥7 *ያስተምሯችኋል፤* ጻድቅ እንደሚሠቃይ፣ ክፉዎች ደግሞ በምቾት እንደሚኖሩ ማለት ነው።

12፥9 *የእግዚአብሔር፤* በኢዮብና በወዳጆቹ ንግግር ሁሉ (ም 3-37)፣ "እግዚአብሔር" (በዕብራይስጥ ያህዌ) የሚለው መለኮታዊ ስም የተጠቀሰው በዚህ ስፍራ ብቻ ነው።

*12፥11፤* ኤሊሁም በ34፥3 ላይ ይህንኑ ተናግሮአል። በ6፥6 ላይ ኢዮብ የኤልፋዝን ንግግር "የማይጣፍጥ ምግብ ነው" ካለው ጋር ያነጻጽሩ።

*12፥12፤* መካሪዎቹ አዛውንት ቢሆኑም እንኳን እውነተኛ ጥበብ የጎደላቸው በመሆናቸው ኢዮብ ይገሥጻቸዋል።

*12፥13-25፤* የዚህ ክፍል ዐቢይ ሐሳብ በቍ 13 ላይ ተመልክቶአል፤ እግዚአብሔር በተፈጥሮ ላይ በተለይም በታሪክ ላይ የበላይ ገዢ ነው። የቀረው ቅኔ የእግዚአብሔርን ኀይልና ጥበብ አሉታዊ በሆነ መልክ ይገልጻል፤ ለምሳሌም ተፈጥሮ ምን ያህል አጥፊ እንደ ሆነ (ቍ 14-15)፣ ዳኞች ምን ያህል አላዋቂዎች እንደ ሆኑ (ቍ 17)፣ ካህናት ምን ያህል እንደ ተዋረዱ (ቍ 19)፣ *ታማኝ* የሆኑት መካሪዎች እንዴት ጸጥ እንዲሉ እንዴት እንደተደረገና ሽማግሌዎችም ማስተዋልን እንደምን እንደ ተነጠቁ (ቍ 20)። እግዚአብሔር ኀያል ሥልጣኑን የሚገልጸው እኛ ልንገነዘበው በምንችለው መንገድ ነው የሚለውን የኤልፋዝን አመለካከት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (5፥10-16)።

*12፥20፤* የቀሩ 2 ማብ ይመ።

*12፥21፡24፤* በዕብራይስጡ ትርጕም እነዚህ ስንኞች በመዝ 107፥40 ላይ ተደግሞአል።

*12፥22፤* ጥልቅ የሆኑ ነገሮች፣ ምስጢሮችና ክፉ ዕቅዶች በእግዚአብሔር ፊት የተገለጡ ናቸው።

12፥25 *ጨለማ በዳበሳ፤* በ5፥14 ላይ ኤልፋዝ በሙሉ ልብ የተናገረውን፣ ኢዮብ ያንኑ በማስመሰል ይህን ክፍል ይደመድማል።

*13፥1-12፤* ኢዮብ መካሪዎቹ ከቶ የማይታመኑ እየሆኑ መምጣታቸውን ይገልጻል (ቍ 12 ይመ)፤ ሐሰተኛ ሐኪሞች ይላቸዋል፤ እግዚአብሔር ከኢዮብ ይልቅ ብርቱ ስለሆነ በኢዮብ ላይ የሐሰት ቃል በመናገር ለእግዚአብሔር በማድላታቸው ይከሳቸዋል (ቍ 7-8)፣ አንድ ቀን እግዚአብሔር ስለ አታላይነታቸው ይቈጣቸዋል (9-11 ይመ)።

13፥1 *ይህን ሁሉ፤* በም 12 ላይ እንደ ተገለጸው የእግዚአብሔርን ሁለገብ ድርጊት የሚያመለክት ነው።

*13፥2፤* 15፥9 ይመ። *ከእናንተ የማንስ አይደለሁም፤* 12፥3 ላይ ያለው እዚህ ተደግሞአል።

*መነጋገር እፈልጋለሁ፤*
ከእግዚአብሔርም ጋር መዋቀስ እሻለሁ::
[4]እናንተ ግን፣ በሐሰት የምትለብጡ ናችሁ፤
ሁላችሁ የማትረቡ ሐኪሞች ሆናችኋል::
[5]ምነው ዝም ብትሉ!
ያ ከጥበብ ይቈጠርላችሁ ነበር!
[6]እንግዲህ ክርክሬን ስሙ፤
የከንፈሬንም አቤቱታ አድምጡ::
[7]ስለ እግዚአብሔር ብላችሁ በክፋት
ትናገራላችሁን?
ስለ እርሱስ በማታለል ታወራላችሁን?
[8]ለእርሱ ታደላላችሁን?
ስለ እግዚአብሔር ጥብቅና ልትቆሙ ነውን?
[9]እርሱ ቢመረምራችሁ መልካም ነገር
ይገኝባችኋልን?
ሰውን እንደምታታልሉ፣ ልታታልሉት
ትችላላችሁን?
[10]በስውር አድልዎ ብታደርጉ፣
በእርግጥ እርሱ ይገሥጻችኋል::
[11]ግርማው አያስደነግጣችሁምን?
ክብሩስ አያስፈራችሁምን?
[12]ምሳሌዎቻችሁ የዐመድ ምሳሌዎች
ናቸው፣
መከላከያቻችሁም የጭቃ ምሽግ ነው::

[13]"ዝም በሉ፤ እኔ ልናገር፤
የመጣው ይምጣብኝ::
[14]ሥጋዬን በጥርሴ፣
ሕይወቴንም በእጄ ለምን እይዛለሁ?
[15]ቢገድለኝም እንኳ በእርሱ ተስፋ
አደርጋለሁ፤
ስለ መንገዴም ፊት ለፊት
እከራከረዋለሁ::[f]
[16]ኀጢአተኛ በእርሱ ፊት መቅረብ
ስለማይችል፤
ይህ ድፍረቴ ለመዳኔ ይሆናል::
[17]ቃሌን በጥንቃቄ አድምጡ፤
እኔ የምለውንም ጆሮአችሁ በሚገባ
ይስማ፤
[18]እንግዲህ ጉዳዬን ይገዩ ቀርቤአለሁ፤
እንደሚፈርድልኝም ዐውቃለሁ::
[19]ሊከሰኝ የሚችል አለ?
ካለም፣ ዝም ብዬ ሞቴን እጠብቃለሁ::
[20]"አምላክ ሆይ፣ እነዚህን ሁለት ነገሮች
ብቻ ስጠኝ፣
ያን ጊዜ ከፊትህ አልሰወርም፤
[21]እጅህን ከእኔ ላይ አንሣ፤
በግርማህም አታስፈራራኝ፤
[22]ከዚያ በኋላ ጥራኝ፤ እኔም
እመልስልሃለሁ፤
ወይም እኔ ልናገር፤ አንተ መልስልኝ::
[23]በደሌና ኀጢአቴ ምን ያህል ነው?
መተላለፌንና ኀጢአቴን አስታውቀኝ::
[24]ፊትህን ለምን ትሰውራለህ?
እንደ ጠላትህስ ለምን ትቈጥረኛለህ?
[25]ነፋስ ያረገፈውን ቅጠል ታስጨንቃለህን?
የደረቀውንስ እብቅ ታሳድዳለህን?
[26]መራራ ነገር ትጽፍብኛለህ፤
የወጣትነቴንም ኀጢአት ታወርሰኛለህ::
[27]እግሬን በእግር ግንድ ታጣብቃለህ፤
ውስጥ እግሬም ላይ ምልክት አድርገህ፣
ዱካዬን አጥብቀህ ትከታተላለህ::
[28]"እንደ በሰበሰ ግንድ፣
ብል እንደ በላው ልብስ፣ ሕይወት
እያደር ማለቅ ነው::

# 14

"ከሴት የተወለደ ሰው፣
ዘመኑ አጭርና በመከራ
የተሞላ ነው፤

13፥1 ኢዮ9፥24
13፥2 ኢዮ12፥3
13፥3 ኢዮ5፥8፡ 17፤9፥14-20፥10፥2፤ 40፥2
13፥4 ኢዮ6፥15፤ መዝ119፥69፤ኢሳ9፥ 15፤ኤር8፥22፤23፥32
13፥5 ቍ13፤መሳ 18፥19፤ምሳ17፥28
13፥6 ኢዮ33፥1፤ 36፥4
13፥7 ኢዮ12፥16፤ 16፥17
13፥8 ዘሌ19፥15
13፥9 ኢዮ9፥3፤ 12፥16፤ገላ6፥7
13፥10 ዘሌ19፥15፤ 2ዜና19፥7
13፥11 ዘፀ3፥6፤ኢዮ 31፥23
13፥12 ነህ4፥2-3
13፥13 ቍ5፤ኢዮ 7፥11፤9፥21
13፥14 መሳ9፥17
13፥15 ኢዮ5፥8፤7፥ 6፤27፥5፤መዝ23፥4፤ 27፥1፤ምሳ14፥32፤ ኢሳ12፥2፤ዳን3፥28
13፥16 ዘፍ3፥8፤ ኢዮ8፥13፤መዝ30፥5፤ ኢሳ12፥1፤54፥7-8፤ ሆሴ14፥4፤ፊል1፥19
13፥17 ኢዮ21፥2
13፥18 ቍ3፤ኢዮ2፥ 3፤9፥21፤23፥4፤ 37፥19
13፥19 ኢዮ3፥13፤ 9፥15፤10፥8፤40፥4፤ ኢሳ50፥8፤ሮሜ8፥33
13፥21 ዘፀ9፥3፤ኢዮ 6፥4፤ዕብ10፥31
13፥22 ኢዮ9፥16፡ 35፥14፥15
13፥23 1ሳሙ26፥ 18፤ኢዮ7፥21፤9፥21፤ 14፥17፤33፥9
13፥24 ዘዳ32፥20፤ ኢዮ16፥9፤19፥11፤ 33፥10፤ መዝ88፥14-15፤ኤር30፥14፤ሰቆ2፥5 13፥25 ዘሌ26፥36፤ኢዮ19፥2፡ 22፡28፤21፥18፤መዝ1፥4፤35፥5፤83፥13፤ኢሳ17፥13፤42፥3፤43፥17፤ ሆሴ13፥3 13፥26 ኢዮ18፥7፤20፥11፤21፥23፤መዝ25፥7 13፥27 ዘፍ40፥15፤ኢዮ10፥14፤33፥11፤ኤር20፥2፤ሐሥ16፥24 13፥28 ዘዳ 28፥35፤መዝ39፥11፤102፥26፤ኢሳ50፥9፤51፥8፤ሆሴ5፥12፤ማር2፥21፤ ያዕ5፥2 14፥1 ዘፍ3፥17፤ኢዮ7፥2፤10፥20፤15፥14፤ማቴ11፥11

[f]15 *ወይም በእርግጥ እርሱ ይገድለኛል፤ ተስፋ የለኝም፤ ይሁን እንጂ ...*

*13፥5፤* ቍ 13 ይመ:: የኢዮብ ወዳጆች ቀደም ሲል አፋቸውን ሳናርፈው አጠገቡ በመገኘታቸው፣ የወዳጅ ተግባር አከናውነዋል (2፥13 ይመ)፤ በዚህ ጊዜ ኢዮብ የሰጠው መልስ ግን ሆን ተብሎ የተሰነዘረ አሽሙር ነው (ከምሳ 17፥28 ጋር ያነጻጽሩ)::

13፥12 *ምሽግ፤ ያዋጣናል* ብለውና የእግዚአብሔር ፍርድ ነው በማለት ያቀረቡት መከላከያ ሐሳባቸው ነው::

*13፥15፤* ከዚህና በቍ 18 ላይ በአማርኛ በቀረበው ጥቅስ ላይ የተመለከተው ሐሳብ ኢዮብ እጅግ የከፋ ሥቃይ ተቀብሎ ሳለ፣ ወዳጆቹ ቢያዋክቡትም፣ ይህ የእግዚአብሔር ሰው ከዚህ ሁሉ ነጻ እንደሚወጣና በመጨረሻም የጌታን ቸርነት እንደ ሚያገኝ ከልብ ያምናል::

13፥16 *ለመዳኔ ይሆናል፤* በፊል1፥19 ላይ ጳውሎስ የኢዮብን ልምድ የሚያስታውስ ይመስላል::

*13፥17፤* በ13፥20-14፥22 ባለው ክፍል ኢዮብ በእግዚአብሔር ፊት መናገር የሚፈልገውን ነገር ወዳጆቹ እንዲያዳምጡ ይጠይቃቸዋል::

13፥20 *ሁለት ነገሮች፤* እግዚአብሔር ሁለት ነገሮችን እንዲያደርግ ኢዮብ ይፈልጋል፤ (1) ጌታ የቅጣት እጁን እንዲያነሣለት (ቍ 21)፣ (2) ከእርሱ ጋር መልካም ግንኙነት እንዲኖረው (ቍ 22)::

*13፥21፤* 9፥34 ይመ::

*13፥23፤* እዚህ ላይ የኢዮብ ቃል መሠረት ያደረገው፣ ምን ጊዜም ሥቃዩ የኀጢአት ውጤት ነው የሚለውን የመካሪዎቹን ሐሳብ ነው:: ነገር ግን እግዚአብሔር በእርሱ ሥቃይ ታላቅ ዐላማ እንዳለው አልተረዳም ነበር:: *በደሌና፣... መተላለፌንና ኀጢአቴን፤* በብሉይ ኪዳን ኀጢአትን ለመግለጽ የገቡ ሦስት ዐበይት ቃላት ናቸው (የዘጸ 34፥7 ማብ ይመ)::

13፥24 *ፊትህን ለምን ትሰውራለህ?* በረከትህ እንዳይወርድ አድርገሃል (የመዝ 13፥1 ማብ ይመ)::

13፥25 *ነፋስ ያረገፈውን ቅጠል —የደረቀውንስ እብቅ፤* የመዝ 1፥4 ማብ ይመ::

13፥26 *የወጣትነቴንም ኀጢአት፤* ኢዮብ በዚህ ጊዜ ኀጢአት እንደሌለበት፣ አሁን ግን እግዚአብሔር የወጣትነት ዘመን ኀጢአቱን እንደቈጠረበት ያስባል:: *ነገር ትጽፍብኛለህ፤* መዝ 130፥3፤ ሆሴ 13፥12 ይመ፤ ከ1ቆሮ 13፥5 ጋር ያነጻጽሩ::

*13፥27፤ እግሬን በእግር ግንድ ታጣብቃለህ፤* ከዚህ ቈየት ብሎ ኤሊሁ የኢዮብን ንግግር ጠቅሶአል (33፥11 ይመ):: *ውስጥ እግሬም ላይ ምልክት፤* በአንድ ሺህ ስምንት መቶ ዓ.ቅ.ክ የነበረው የባቢሎን ንጉሥ፣ የሐሙራቢ ሕግ በባሪያዎች ላይ ምልክት ይደረግ እንደ ነበረ ያረጋግጣል:: ኢዮብ፣ እግዚአብሔር ከማረከው በኋላ ሥቃይ ውስጥ አስገብቶት እንደሚያስፈራራው ይሰማዋል (ቍ 25 ይመ)::

*13፥28-14፥11* የሰው ዕድል ፈንታው መከራ፣ መጨረሻውም ሞት እንደሆነ ለሚገልጸው ለም 14 የተሰጠ መግቢያ ነው::

13፥28 *ብል እንደ በላው ልብስ፤* ማቴ 6፥19-20፤ ሉቃ 12፥33 ይመ::

*14፥1፤* 5፥7 ይመ::

2እንደ አበባ ይፈካል፤ ይረግፋልም፤
እንደ ጥላ ይፈጥናል፤ አይጸናምም።
3እንደዚህ ባለ ሰው ላይ ዐይንህን
ታሳርፋለህን?
ለፍርድስ በፊትህ ታቀርበዋለህን?[ፍ]
4ከርኩስ ነገር ውስጥ ንጹሕን ማን ሊያወጣ
ይችላል?
አንድ እንኳ የሚችል የለም!
5የሰው ዕድሜ አስቀድሞ የተወሰነ ነው፣
የወራቱንም ብዛት ወስነህ አስቀምጠሃል፤
ሊያልፈው የማይችለውንም ገደብ
አኖርህለት።
6እንግዲህ ዘመኑን እንደ ምንደኛ
እስኪፈጽም ድረስ፣
ፊትህን ከእርሱ መልስ፤ ተወው።
7"ዛፍ እንኳ ቢቈረጥ፣
እንደ ገና ሊያቈጠቍጥ፣
አዳዲስ ቅርንጫፍም ሊያበቅል ተስፋ
አለው።
8ሥሩ በምድር ውስጥ ቢያረጅ
ጕቶው በመሬት ውስጥ ቢበሰብስም፣
9የውሃ ሽታ ባገኘ ጊዜ ያቈጠቍጣል፤
እንደ ተተከለም ችግኝ ቅርንጫፍ
ያወጣል።
10ሰው ግን ይሞታል፤ ክንዱንም
ይንተራሳል፤
ነፍሱም ትወጣለች፤ ከእንግዲህስ የት
ይገኛል?
11ውሃ ከባሕር ውስጥ እንደሚያልቅ፣
የወንዝ ውሃም ጠፍቶ እንደሚደርቅ፣
12እንደዚሁም ሰው ይተኛል ቀናም
አይልም፤
ሰማይ እስከሚያልፍ ድረስ አይነቃም፤
ከእንቅልፋም አይነሣም።
13"ምነው መቃብር[ፐ] ውስጥ በሰወርኸኝ!
ቍጣህም እስከሚያልፍ በሸሸግኸኝ!
ምነው ቀጠሮ ሰጥተህ፣
ከዚያ በኋላ ባስታወስኸኝ!
14ሰው ከሞተ በኋላ ተመልሶ በሕይወት
ይኖራል?
እድሳቴ[ገ] እስከሚመጣ ድረስ፣

14፥2 ኢዮ4፥20፥8፥9፤መዝ37፥2፤39፥4፤49፥12፤90፥5-6፤102፥11፤103፥15፤109፥23፤144፥4፤መክ6፥12፤ኢሳ40፥6-8፤ያዕ1፥10
14፥3 ኢዮ7፥18፤መዝ8፥4፤144፥3
14፥4 ኢዮ4፥17፤9፥30፤መዝ51፥10፤ዮሐ3፥6፤ሮሜ5፥12፤7፥14፤ኤፌ2፥1-3
14፥5 ኢዮ21፥21፤24፥1፤መዝ31፥15፤39፥4፤90፥12፥139፥16፤ሐሥ17፥26
14፥6 ኢዮ7፥1:2:19፤መዝ39፥13፤ኢሳ16፥14፤21፥16
14፥7 ኢዮ19፥10፤24፥20፤መዝ52፥5፤ኢሳ6፥13፤11፥1፤53፥2፤60፥21
14፥8 ኢሳ6፥13፤11፥1፤53፥2
14፥9 ዘሌ26፥4፤ኢዮ29፥19፤መዝ1፥3፤ኤር17፥8፤ሕዝ31፥7፤34፥27፤ዘካ10፥1
14፥10 ቍ12፤ኢዮ10፥21፤13፥19
14፥11 2ሳሙ14፥14
14፥12 ቍ10፤መዝ102፥26፤ሐሥ3፥21፤ራእ20፥11፤21፥1
14፥13 ዘፍ8፥1፤ኢዮ6፥8፤7፥9፤መዝ30፥5፤ኢሳ26፥20፤54፥7
14፥14 2ነገ6፥33፤ኢዮ7፥1
14፥15 ኢዮ10፥3፤13፥22
14፥16 ኢ10፥4:6፤መዝ139፥1-3፤ምሳ5፥21፤ኤር16፥17፤32፥19፤1ቆሮ13፥5
14፥17 ዘዳ32፥34፤ኢዮ9፥30፤13፥23፤ኤር32፥10
14፥18 ኢዮ18፥4፤ሕዝ38፥20
14፥19 ዘፍ7፥23፤ኢዮ7፥6፤ሕዝ13፥13
14፥20 ኢዮ4፥20፤7፥10፤8፥18፤12፥9፤27፥19፤ያዕ1፥10

ተጋድሎ የሞላበትን ዘመኔን ሁሉ
እታገሣለሁ።
15ትጠራኛለህ፤ እኔም እመልስልሃለሁ፤
የእጅህንም ሥራ ትናፍቃለህ።
16በዚያን ጊዜ በእርግጥ እርምጃዬን
ትከታተላለህ፤
ነገር ግን ኀጢአቴን አትቈጣጠርም።
17መተላለፌ በከረጢት ይጳጠራል፤
ኀጢአቴንም ትሸፍናለህ።
18"ተራራ እንደሚሸረሸርና
እንደሚወድቅ፣
ዐለትም ከስፍራው እንደሚወገድ፣
19ውሃ ድንጋይን እንደሚበረብር፣
ጐርፍም ዐፈርን አጥቦ እንደሚወስድ፣
አንተም የሰውን ተስፋ ታጠፋለህ።
20አንድ ጊዜ ፈጽመህ ትበረታለህ፤ እርሱም
ያልፋል፤
ገጽታውን ትቀይራለህ፤ ትሸኘዋለህም።
21ልጆቹ ቢከበሩ አያውቅም፤
ቢዋረዱም አያይም።
22የገዛ አካሉ ሕመም ብቻ ይሰማዋል፤
ለራሱም ብቻ ያለቅሳል።"

## ኤልፋዝ

# 15

ቴማናዊው ኤልፋዝ እንዲህ ሲል መለሰ፤
2"ጠቢብ ሰው በከንቱ ንግግር መልስ
ይሰጣልን?
ወይስ በምሥራቅ ነፋስ ሆዱን ይሞላል?
3በማይረባ ቃል፣
ፍሬ ቢስ በሆነም ንግግር ይከራከራልን?
4አንተ ግን እግዚአብሔርን መፍራት
ታጣጥላለህ፤
አምልኮተ እግዚአብሔርን ትከለክላለህ።
5ኀጢአትህ አፍህን ታስተምረዋለች፤
የተንኰለኞችንም አነጋገር መርጠህ
ትይዛለህ።

14፥21 ኢዮ21፥21፤መክ9፥5፤ኢሳ63፥16 14፥22 ኢዮ21፥21፤መዝ38፥7፤ኢሳ21፥3፤ኤር4፥19 15፥1 ኢዮ4፥1

[ፍ]3 ሰብዓ ሊቃናት፣ ቩልጌትና ሱርስት እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ - ግን *ታቀርበኛለህን?* ይላል
[ፐ]13 በዕብራይስጥ *ሲኦል* ማለት ነው
[ገ]14 ወይም *መፈታቴ*

*14፥2-6፤* በቍ 4 እና 2 ላይ የተመሠረተ ባለ አቻ ስንኝ ሲሆን፣ ከቍ 5 እና ከቍ 3 እስከ 6 ካለው ክፍል ጋር ተመሳሳይነት አለው። ኢዮብ ከእግዚአብሔር ጋር ክርክር የሚገጥም ይመስላል፤ በሰው ቍጥር ውስጥ የማይገባና ከማሕፀንም ጀምሮ ንፁሕ ካልሆነ፣ ታዲያ ይህን ያህል ለምን ታተኵርበታለህ (13፥25 ይመ)?

14፥2 *ይረግፋልም፤* ሕይወት ቅጽበታዊና ጠፊ ናት (8፥19፤ መዝ 37፥2፤ ኢሳ 40፥7:24 ይመ)። *እንደ ጥላ ይፈጥናል፤* የ8፥9 ማብ ይመ።

*14፥7-12፤* ሰው፣ ከተቈረጠ በኋላ እንኳ ተመልሶ እንደሚለመልም ዛፍ ሳይሆን፣ ለአጭር ጊዜ ታይቶ እንደሚጠፋ አበባ ነው (ቍ 2)።

14፥7 *ሊያቈጠቍጥ፤* ለዚህ ቃል በቍ 14 ላይ የተሰጠው የዕብራይስጡ ትርጕም "መታደስ" የሚል ነው።

*14፥13-17፤* በዚህ ጊዜ የኢዮብ መንፈስ በሰውነቱ መበስበስ ምክንያት ተስፋ ከመቍረጥ ደረጃ በላይ የደረሰ ይመስላል። ከዚህ ላይ የትንሣኤን ምንነት የሚያስረዳ ትምህርት ሙሉ በሙሉ አልተሰጠም፤ ነገር ግን እግዚአብሔር ፈቃዱ ከሆነ፣ የሕይወት ባለቤት የሆነው ጌታ፣ ኢዮብን በመቃብር ውስጥ በመደበቅ፣ የመለኮት ቍጣ ሲበርድ ወደ ሕይወት ሊመልሰው እንደሚችል ኢዮብ ያስባል።

14፥14 *ተጋድሎ የሞላበትን ዘመኔን፤* የ7፥1 ማብ ይመ።

*14፥18-22፤* ኢዮብ ጽልመታዊ ከሆነ አመለካከት ላይ የደረሰው፣ ትንሣኤ ሙታን እንደሚኖር ከመጠራጠር የተነሣ ሳይሆን፣ ሕይወቱ በሥቃይና በሐዘን ተሞልቶ እያለ፣ እግዚአብሔር እርሱን ለመታደግ ፈቃደኛ ስላልመሰለው ነው።

*15፥1-6፤* እስካሁን ድረስ ከሦስቱ መካሪዎች የመጀመሪያው ርኅሩኅ ኤልፋዝ ነበር። ከዚህ በኋላ ግን ትዕግሥቱ ስላለቀ ከመቼውም ጊዜ ይልቅ ኢዮብን ይቃወማል።

15፥2 *በከንቱ፤* ኢዮብ ኤልፋዝን በብርቱ ቃል ለተናገረበት በ16፥3 ላይ ለሰፈረው ሐሳብ፣ የተሰጠው የዕብራይስጥ ትርጕም፣ "አሰልቺ" የሚል ነው። *በምሥራቅ ነፋስ፤* 27፥21፤ 38፥24 ይመ። ከበረሃ የሚነሣ ነፋስ (ሲራኮ የተባለ) ነው (የዘፍ 41፥6፤ የኤር 4፥11 ማብ ይመ)።

15፥4 *እግዚአብሔርን መፍራት፤* የ4፥6 ማብ ይመ።

*15፥5፤* ማቴ 15፥11:17-18 ይመ።

[6]የሚፈርድብህ አንደበትህ እንጂ እኔ
አይደለሁም፤
የሚመሰክርብህም እኔ ሳልሆን የገዛ
ከንፈርህ ነው።
[7]"ለመሆኑ ከሰው ሁሉ ቀድመህ የተወለድህ
አንተ ነህን?
ወይስ ከኰረብቶች በፊት ተገኝተሃል?
[8]በእግዚአብሔር የመማክርት ጉባኤ ላይ
ነበርህን?
ጥበብስ የተሰጠው ለአንተ ብቻ ነው?
[9]እኛ የማናውቀው አንተ ግን የምታውቀው
ምን ነገር አለ?
እኛስ የሌለን አንተ ያለህ ማስተዋል የቱ
ነው?
[10]በዕድሜ ከአባትህ የሚበልጡ፤
የሸበቱ ሽማግሌዎች ከእኛ ጋር አሉ።
[11]የእግዚአብሔር ማጽናናት፤
በርጋታ የተነገረህ ቃል አነሰህን?
[12]ልብህ ለምን ይሸፍታል?
ዐይንህንስ ምን ያጕረጠርጠዋል?
[13]በእግዚአብሔር ላይ እንድትቈጣ፤
እንደዚህ ያለ ቃል ከአፍህ እንዲወጣ
ያደረገህ ምንድን ነው?
[14]"ንጹሕ ይሆን ዘንድ ሰው ምንድን ነው?
ጻድቅስ ይሆን ዘንድ፤ ከሴት የተወለደ
ምንድን ነው?
[15]እነሆ፤ እግዚአብሔር በቅዱሳኑ እንኳ
አይታመንም፤
ሰማያትም በእርሱ ፊት ንጹሓን
አይደሉም።
[16]ታዲያ፤ ክፋትን እንደ ውሃ የሚጠጣ!
አስጸያፊና ርኩስ ሰውማ እንዴት ይታመን!
[17]"አድምጠኝ፤ በግልጽ አስረዳሃለሁ፤
ያየሁትንም እነግርሃለሁ፤
[18]ጠቢባን ከአባቶቻቸው የተቀበሉትን፤
ሳይሸሽጉ የተናገሩትን አስረዳሃለሁ፤
[19]ምድሪቱ ለአባቶቻቸው ተሰጠች፤
በመካከላቸውም ባዕድ አልተቀመጠም፤
[20]ክፉ ሰው ዕድሜውን ሙሉ፤
ጨካኙም በተመደበለት ዘመን ሁሉ
ይሠቃያል።
[21]የሚያስደነግጥ ድምፅ በጆሮው ላይ
ይጮኻል፤
በሰላም ጊዜ ቀማኞች አደጋ
ያደርሱበታል።
[22]ከጨለማ ወጥቶ ማምለጥ
ይፈራል፤
ለሰይፍም የተመደበ ነው።
[23]የአሞራ እራት[ጣ] ለመሆን ይቅበዘበዛል፤
የጨለማ ቀን መቅረቡን ያውቃል።
[24]ጭንቀትና ሐዘን ያስፈሩሩታል፤
ለማጥቃት እንደ ተዘጋጀ ንጉሥም
ያይሉበታል፤
[25]እጁን በእግዚአብሔር ላይ አንሥቶአልና፤
ሁሉን የሚችለውን አምላክም ደፍሮአል፤
[26]ወፍራምና ጠንካራ ጋሻ አንግቦ፤
ሊቋቋመው ወጥቶአል።
[27]"ፊቱ በስብ ቢሸፈን፤
ሽንጡ በሥጋ ቢደነድንም፤
[28]መኖሪያው በፈራረሱ ከተሞች፤
የፍርስራሽ ክምር ለመሆን በተቃረቡ፤
ሰው በማይኖርባቸው ወና ቤቶች ውስጥ
ይሆናል።
[29]ከእንግዲህ ባለ ጠጋ አይሆንም፤ ሀብቱም
አይቈይም፤
ይዞታውም በምድር ላይ አይሰፋም።
[30]ከጨለማ አያመልጥም፤
ቅርንጫፎቹን ነበልባል ያደርቃቸዋል፤
በእግዚአብሔርም እስትንፋስ ይወሰዳል።

15፥2 ዘፍ41፥6 15፥3 ነህ4፥2-3፤ ኢዮ6፥26 15፥4 ኢዮ25፥6 15፥5 ኢዮ5፥13፤ 11፥6፤22፥5፤ምሳ 16፥23 15፥6 ኢዮ9፥15፤ 18፥7፤መዝ10፥2፤ማቴ12፥37፤ሉቃ19፥22 15፥7 1ሳሙ2፥8፤ ኢዮ38፥21፤መዝ90፥2፤ምሳ8፥25 15፥8 ኢዮ12፥2፤ 29፥4፤ኢሳ9፥6፤40፥13፤41፥28፤ኤር23፥18፤ሮሜ11፥34፤ 1ቆሮ2፥11 15፥9 ኢዮ12፥3 15፥10 2ዜና10፥6፤ኢዮ12፥12 15፥11 ዘፍ37፥35፤ ዘጸ8፥3፤32፥39፤ኢዮ 5፥17፤6፥10፤22፥22፤ 23፥12፤36፥16፤መዝ 119፥11፡72፤ኤር15፥16፤ዘካ1፥13፤2ቆሮ 1፥3-4 15፥12 ኢዮ11፥13፤ 36፥13 15፥13 ኢዮ11፥8፤ 22፥5፤32፥3፤መዝ94፥4፤ምሳ29፥11፤ዳን 11፥30 15፥14 2ዜና6፥36፤ ኢዮ4፥17፤14፥1 15፥15 ኢዮ4፥18፤ 5፥1 15፥16 ዘሌ5፥2፤ ኢዮ 4፥19፤12፥4፤ 20፥12፤34፥7፤መዝ 14፥1፤ምሳ19፥28 15፥17 ኢዮ4፥8 15፥18 ዘጸ32፥7 15፥19 ዘፍ12፥1፤ ኢዮ22፥8 15፥20 ቍ 24፥ኢዮ 24፥1፤27፥13-23፤ኢሳ 2፥12፤8፥22፤50፥11፤ 66፥24፤ኤር46፥10፤ አብ1፥15፤ሰፎ1፥7 15፥21 ቍ 24፤ 1ሳሙ3፥11፤ኢዮ18፥ 11፤20፥25፤22፥10፤ 27፥20፤ኢሳ13፥3፤ ኤር6፥25፤20፥3፤ 51፥25፡53፡56፤1ተሰ5፥3 15፥22 ቍ 23፤ኢዮ5፥14፤16፥13፤18፥19፤19፥29፤20፥24፤24፥17፤27፥14፤33፥18፤36፥12፤38፥15፤መዝ 91፥5፤ምሳ7፥23፤መሓ3፥8፤ኢሳ1፥20፤ኤር44፥27፤ሆሴ9፥13፤አሞ 5፥19 15፥23 ቍ 22፤ኢዮ18፥12፤መዝ109፥10፤ምሳ30፥17፤ሕዝ 39፥17፤ማቴ24፥28፤ሉቃ17፥37 15፥24 ቍ 20፤ኢዮ18፥14፤ኢሳ 8፥22፤9፥1 15፥25 ኢዮ11፥8፤35፥12፤36፥9፤40፥8፤መዝ2፥2-3፤ 44፥16፤73፥9፤75፥5፤ምሳ21፥30፤ኢሳ3፥16፤10፥32፤37፥23፤45፥9 15፥26 ኤር44፥16 15፥27 መሳ3፥17 15፥28 ኢዮ3፥14፤ኢሳ 5፥9 15፥29 ኢዮ3፥15፤7፥8፤ኢሳ5፥8 15፥30 ቍ 32፡34፤ዘዐ15፥ 10፤ኢዮ5፥14፤8፥19፤16፥7፤18፥16፤20፥26፤22፥20፤29፥19፤31፥12፤ ኢሳ40፥23-24፤ሆሴ9፥1-16፤ሚል4፥1 15፥31 ኢዮ20፥7፤22፥13፤ 27፥9፤31፥5፤

[ጣ]23 ወይም ለአሞራ እራት ለመፈለግ

15፥6 *የሚፈርድብህ አንደበትህ፤* 9፥20 ይመ።

*15፥7-10፤* ኢዮብ ራሱን እንደ ሰማይ መላእክት ጠቢብ አድርጎ እንደሚቈጥር (የ1፥6 ማብ ይመ)፤ እውነቱ ሲታይ ግን ከተራ ሰው እንኳ የማይሻል እንደሆነ ኤልፋዝ ይናገራል።

*15፥10፤* በዕድሜ ብዛት ብዙ ልምድ ስለሚገኝ፤ በጥንት ጊዜ ዕድሜ እንደ ጥበብ ይቈጠር ነበር፤ ይህ እውነት ግን በኢ ሊሁ ዘንድ ተቀባይነት አልነበረውም (32፥6-9 ይመ)።

*15፥11-13፤* እንደ ኤልፋዝ አመለካከት ከሆነ፤ የኢዮብ ወዳጆች እርሱን ያጽናኑት ዘንድ እግዚአብሔር የላካቸው ናቸው (ቍ 11)፤ እነርሱ ወዳጃቸውን ለማጽናናት መጥተው ሳለ፤ ኢዮብ በቍጣ በመመለሱ ኤልፋዝ ኢዮብን ይገሥጸዋል፤ ይሁን እንጂ ኤልፋዝ መሰሪ በመሆኑ ከበደል ነጻ አልነበረም (ም 5)፤ የቀሩት ሁለቱ መካሪዎችም የባሰውን መሰሪዎች ነበሩ። ኢዮብን ለማ ጽናናት ያላንጻች ሽፍጥ የተለገሰው ምክር በትክክል ሲታይ ግምት ውስጥ የሚገባ አልነበረም (4፥2-6 ይመ)።

*15፥14-16፤* 25፥4-6 ይመ። ኤልፋዝ ምናልባት እግዚአ ብሔር በመገለጥ ሰጥቶኛል ብሎ በማሰቡ ሳይሆን አይቀርም፤ ቀደም ሲል በ4፥17-19 ላይ የተናገረውን እዚህ ላይ የደገመው (የ4፥12-21 ማብ ይመ)።

15፥14 *ከሴት የተወለደ፤* ኢዮብ በ14፥1 ላይ የተናገረውን እዚህ ላይ ይደግመዋል።

15፥15 *በቅዱሳኑ፤* መላእክት ናቸው (የ5፥1 ማብ ይመ)።

15፥16 *ክፋትን እንደ ውሃ የሚጠጣ፤* በ34፥7 ላይ ኤሊሁ ስለ ኢዮብ የተናገረውን ይመ።

*15፥17-26፤* ኤልፋዝ ቀደም ሲል ሰጥቶት የነበረውን ከጥንት ሲወርድ ሲዋረድ የመጣ ምክር አሁንም ይደግፋል፤ ይኸ ውም ክፉ ሰው (ኢዮብን ማለቱ ነው) የሚገባውን መከራ ከቶ ሊያመልጠው አይችልም የሚል ነው።

*15፥20-35፤* የክፉውን ሰው ዕጣ ፈንታ የሚያመለክት ቅኔ ነው (8፥11-19 ይመ)። ኤልፋዝ የተለያዩ ምሳሌዎችን በመጠ ቀም ምክር መስጠቱን አሁንም ይቀጥላል፤ ይኸውም ከእግዚ አብሔር ጋር የሚጣላውን ሰው (ቍ 24-26)፤ በመጨረሻ ቅጣት የሚገባውን ክፉ ሰው (ቍ 27-32)፤ ገና ሳይበስል ፍሬው የሚረግፈውን ወይን (ቍ 33)፤ አበባው የሚረግፍበትን ወይራ (ቍ 33) እንደ ምሳሌ ተጠቅሞአል። ኤልፋዝ፤ ክፉዎች፤ ተቀ ማጥለው ይኖራሉ የሚለውን የኢዮብን አመለካከት ስለሚቃወም፤ ኢዮብ የጻድቃን መከራ ምስጢሩ ምን እንደ ሆነ በመጠየቅ ከእርሱ ጋር መጨቃጨቅ አልፈለገም።

15፥23፡30 *የጨለማ፤* ሞት ነው፤ ይህም ወደ ሙታን ዓለም የሚደረገውን ጉዞ የሚያሳይ ነው (የ10፥21 ማብ ይመ)።

³¹በአጸፋው እንዳች አያገኝምና፤
ከንቱን ነገር በመታመን ራሱን
አያታልል።
³²ጊዜው ሳይደርስ ይጠወልጋል፤
ቅርንጫፉም አይለመልምም።
³³ፍሬው በጮርቃነት እንደ ተለቀመበት
የወይን ተክል፤
አበባውም እንደ ረገፈበት የወይራ ዛፍ
ይሆናል።
³⁴የዐመፀኞች ጉባኤ ትመክናለች፤
የጉቦ ሰሰኞችም ድንኳን በእሳት
ትበላለች።
³⁵መከራን ይፀንሳሉ፣ ክፋትንም ይወልዳሉ፤
በሆዳቸውም ተንኰል ይጠነስሳሉ።"

## ኢዮብ

**16** ኢዮብም እንዲህ ሲል መለሰ፤
²"ይህን የሚመስል ብዙ ነገር
ሰምቻለሁ፤
እናንተ ሁላችሁ የምታስጨንቁ
አጽናኞች ናችሁ።
³ይህ ከንቱ ንግግር አያልቅምን?
ትለፈልፍ ዘንድ የሚገፋፋህ ምንድን
ነው?
⁴እናንተ በእኔ ስፍራ ብትሆኑ ኖሮ፣
እኔም እንደ እናንተ መናገር እችል
ነበር፤
ቃላት አሳክቼ በመናገር፣
በእናንተ ላይ ራሴን መነቅነቅ በቻልሁ
ነበር።
⁵ይልቁንም እንደበቴ ባበረታታችሁ፣
የከንፈሬም ማጽናናት ባሳረፋችሁ ነበር።
⁶"ብናገር ሕመሜ አይሻለኝም፤
ዝም ብልም አይተወኝም።
⁷እግዚአብሔር ሆይ አሁንስ አድክመኸኛል፤
ወገኖቼንም ሁሉ አጥፍተሃል።
⁸ጭምትርትር ያደረግኸኝ ምስክር
ሆኖብኛል፣
ዐጥንቴን ያወጣው ክሳቴም ያጋልጠኛል።
⁹በቍጣው ሰነጠቀኝ፤ በጥላቻው
አስጨነቀኝ፣
ጥርሱን ነከሰብኝ፤
ባላጋራዬ ክፉ ዐይኑን ተከለብኝ።
¹⁰ሰዎች በፌዝ አፋቸውን ከፈቱብኝ፤
በንቀት ጕንጬን ጠፈጠፉኝ፤
በአንድነትም በላዬ ተሰበሰቡ።
¹¹እግዚአብሔር ለክፉዎች አሳልፎ ሰጠኝ፤
በጠማሞችም እጅ ጣለኝ።
¹²በሰላም እኖር ነበር፤ እርሱ ግን ሰባበረኝ፤
ዐንገቴን ይዞ አደቀቀኝ፤
ማነጣጠሪያ ዒላማው አደረገኝ፤
¹³የእርሱ ቀስተኞች ከበቡኝ፤
ያለ ርኅራኄ ኵላሊቴን ይበጣጥሳል፤
ሐሞቴን መሬት ላይ ያፈስሳል።
¹⁴ደጋግሞ ይቀጠቅጠኛል፤
እንደ ጦረኛም ተንደርድሮ ይመጣብኛል።
¹⁵"በቈዳዬ ላይ ማቅ ሰፍቻለሁ፤
ክብሬን በዐፈር ውስጥ ቀብሬአለሁ።
¹⁶ፊቴ ከልቅሶ የተነሣ ቀልቶአል፤
ጨለማም በዐይኖቼ ቆብ ላይ ዐርፎአል፤
¹⁷ነገር ግን በእጄ ዐመፅ አይገኝም፤
ጸሎቴም ንጹሕ ነው።
¹⁸"ምድር ሆይ፤ ደሜን አትሸፍኚ፤
ጩኸቴም ማረፊያ አያግኝ!
¹⁹አሁን እንኳ ምስክሬ በሰማይ አለ፤
ጠበቃዬም በላይ በአርያም ይገኛል።
²⁰ወዳጆቼ በንቀት ቢመለከቱኝም፣[ወ]
ዐይኔ ወደ እግዚአብሔር ያነባል።
²¹ሰው ለወዳጁ እንደሚማልድ፣
በእግዚአብሔር ፊት የሚማልድ ሰው ምነው
በተገኘ!
²²"ከጥቂት ዓመታት በኋላ፣
ወደማልመለስበት መንገድ እሄዳለሁ።

35፥13፤ምሳ1፥16፤6፥18፤15፥29፤ኢሳ1፥15፤30፥12፤44፥20፤47፥10፤59፥4፡7፤ኤር7፥4፡8፤11፥11፤ሚክ2፥11፤3፥4፤ማቴ6፥19፤ማር13፥5፤ያዕ1፥16
15፥32 ቍ30፤ኢዮ22፥16፤36፥14፤መዝ55፥23፤109፥8፤ምሳ10፥27፤መክ7፥17
15፥33 ኢዮ4፥20፤ዕን3፥17
15፥34 ቍ30፤ዘፀ23፥8፤1ሳሙ8፥3፤ኢዮ8፥13፤ዕብ10፥27
15፥35 ኢዮ4፥8፤5፥7፤ኢሳ29፥20፤ገላ6፥7፤ያዕ1፥15
16፥2 ኢዮ6፥15፤መዝ69፥20
16፥3 ኢዮ6፥26፤11፥2፤18፥2
16፥4 2ነገ19፥21፤መዝ22፥7፤ኢሳ37፥22፤ኤር48፥27፤ሰቆ2፥15፤ሰፎ2፥15፤ማቴ27፥39
16፥5 ዘፍ37፥25፤ኢዮ29፥25
16፥6 ኢዮ6፥3፤7፥21
16፥7 መሳ8፥5፤ኢዮ1፥19፤7፥3
16፥8 ኢዮ10፥17፤17፥7፤19፥20፤33፥21፤መዝ6፥7፤22፥17፤88፥9፤102፥5፤109፥24፤ሰቆ5፥17
16፥9 ኢዮ9፥5፤12፥14፤13፥24፤18፥4፤19፥11፤30፥21፤መዝ35፥16፤37፥12፤112፥10፤ሰቆ2፥16፤ሆሴ6፥1፤ሐሥ7፥54
16፥10 ቍ7፤ኢዮ11፥3፤12፥4፤19፥12፤18፥21፡3፤30፥1፡9፡12፤መዝ22፥13፤27፥3፤35፥15፡21፤69፥12፤119፥51፤ኢሳ50፥6፤ሰቆ3፥30፤ሚክ5፥1፤ሐሥ7፥57፤23፥2
16፥11 ኢዮ9፥24
16፥12 ኢዮ6፥4፤9፥17፤ሰቆ3፥12
16፥13 ኢዮ3፥23፤20፥24፤ምሳ7፥23፤ሰቆ3፥13
16፥14 ኢዮ9፥17፤10፥3፤ኢዩ2፥7
16፥15 ዘፍ37፥34፤ኢዮ2፥8
16፥16 ቍ20፤ኢዮ2፥7፤17፥7፤30፥17፡30፤33፥19፤መዝ6፥6፤ኢሳ52፥14
16፥17 ኢዮ6፥28፤10፥7፤13፥7፤ኢሳ53፥9፤55፥7፤59፥6፤ኤር18፥11፤ዮና3፥8፤ሰፎ3፥13
16፥18 ዘፍ4፥10፤ኢዮ19፥24፤መዝ5፥2፤18፥6፤66፥18-19፤102፥1፤119፥169፤ኢሳ26፥21፤ዕብ11፥4
16፥19 ዘፍ31፥50፤ኢዮ19፥27፤21፥17፤22፥12፤25፥2፤27፥13፤31፥2፤42፥2፤መዝ113፥5፤ኢሳ33፥5፤57፥15፤58፥4፤66፥1፤ማር11፥10፤ሮሜ1፥9፤1ተሰ2፥5
16፥20 ቍ16፤ሰቆ2፥19፤ዮሐ15፥15፤ሮሜ8፥34
16፥21 1ነገ8፥45፤መዝ9፥4፤140፥12
16፥22 ኢዮ10፥21

[ወ]20 ወይም ወዳጆቼ አማላጅ ቢሆኑልኝም

15፥35 *መከራን ይፀንሳሉ፤ ክፋትንም ይወልዳሉ፤* በኢሳ 59፥4 ላይ (ማብ ይመ) ተጠቅሶአል። ክፉ ሐሳብ በልብ ውስጥ ከተስተናገደ፣ ወዲያውኑ ወደ ክፉ ድርጊት ማምራቱ አይቀርም።

*16፥1-5፤* ኢዮብ የወዳጆቹን ምክር አልተቀበለም።

*16፥2-5፤* ጠቃሚ ምክር የተንዛዛና የጭፍን ፍርድ ሳይሆን፣ እጥር ምጥን ያለና የሚያጽናና ነው።

16፥2 *የምታስጨንቁ አጽናኞች፤* የ13፥1-12 ማብ ይመ። ኢዮብ በሦስቱ ወዳጆቹ አይሁን እንጂ በመጨረሻ ተጽናንቶአል (42፥11 ይመ)።

16፥3 *ከንቱ፤* አሰልቺ ማለት ነው የ15፥2 ማብ ይመ።

16፥4 *ራሴን መነቅነቅ፤* የስድብና የንቀት ምልክት ነው (መዝ 22፥7፤ ኤር 48፥27፤ ማቴ 27፥39 ይመ)።

*16፥9፤* እግዚአብሔር እንደ ጨካኝ አንበሳ (10፥16 ይመ) ኢዮብን ሲያጠቃውና ሥጋውንም ሲበጫጭቀው የሚያሳይ ተምሳሌታዊ አገላለጽ ነው። *ጠላት፤* ዕብራይስጡ "ባላጋራ" የሚል ትርጕም አለው (19፥11 ይመ)።

*16፥10-14፤* ኢዮብ ራሱን እንደ እግዚአብሔር ዒላማ ይቈጥራል፤ ያለበትም ሁኔታ ኤልፋዝ በ15፥25-26 ላይ ከተናገረው ጋር ተቃራኒ እንደሆነ ተገንዝቦአል።

16፥12 *በሰላም... እርሱ ግን ሰባበረኝ፤* 2፥3 እና ማብ ይመ። *ማነጣጠሪያ ዐላማው አደረገኝ፤* የ6፥4 ማብ ይመ።

*16፥15-17፤* ኢዮብ ሥቃዩን ሲያጠቃልል፦ ምንም እንኳ በደል ባይኖርበትም ሥቃዩ የቀጠለ መሆኑን ይገልጻል።

16፥15 *ማቅ... በዐፈር፤* የሐዘን ምልክት ነው (የዘፍ 37፥34፤ የዮና 3፥5-6 ማብ ይመ)።

*16፥18-21፤* ቍ 18 (ቍ 22፤ 17፥1 ይመ)፤ ኢዮብ ረጅም ዕድሜ አግኝቶ በወዳጆቹ ዘንድ ከበደል ነጻ መሆኑ የሚታወቅለት አልመሰለውም፤ ነገር ግን በሰማይ ወዳጅ እንዳለው (ቍ 20)፣ ወዳጅም ቅዱስ እንደ ሆነ (5፥1 ይመ)፣ ምስክሩ፣ ጠበቃው፣ በእግዚአብሔር ፊት የሚቆምለትና (ቍ 21 ይመ፤ 9፥33 እና ማብ ይመ) ተስፋውም እርሱ ብቻ እንደ ሆነ ይናገራል።

16፥18 *ደሜን... ጩኸቴም፤* ኢዮብ የራሱ ደም እንደ አቤል ደም (ዘፍ 4፥10 እና ማብ ይመ) ንጹሕ ስለሆነ ከሞተ በኋላ ከምድር እንደሚጮኽ ያስባል።

16፥22 *ከጥቂት ዓመታት በኋላ፤* ኢዮብ ወዲያው እንደሚሞት ተስፋ አድርጎአል። *ወደማልመለስበት መንገድ እሄዳለሁ፤* ወደ መቃብር ማለት ነው (የ7፥9፤ የ10፥21 ማብ ይመ)።

17 መንፈሴ ደክሞአል፣
ዘመኔ አጥሮአል፤
መቃብርም ተዘጋጅቶልኛል።
[2]አላጋጮች ከበውኛል፤
ትኵረቴም ትንኰሳቸው ላይ ነው።
[3]"እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ ተያዥ ሁነኝ፤
ከአንተ ሌላ ዋስ የሚሆነኝ ማን አለ?
[4]እንዳያስተውሉ ልባቸውን ይዘሃል፤
ስለዚህ ድል አትሰጣቸውም።
[5]ለጥቅም ሲል ወዳጆቹን የሚያወግዝ፣
የልጆቹ ዐይን ይታወራል።
[6]"እግዚአብሔር ለሰው ሁሉ መተረቻ፣
ፊቱ ላይ የሚተፋበት ሰውም አደረገኝ።
[7]ዐይኔ ከሐዘን የተነሣ ፈዘዘ፤
መላ አካሌም እንደ ጥላ ሆነ።
[8]ቅኖች በዚህ ነገር ይደነግጣሉ፤
ንጹሓንም በዐመፀኞች ላይ ይነሣሉ።
[9]ጻድቃን ግን በያዙት መንገድ ይጸናሉ፤
ንጹሕ እጅ ያላቸውም እየበረቱ ይሄዳሉ።
[10]"ነገር ግን እናንተ ሁላችሁ፣
እስቲ ተመልሳችሁ እንደ ገና ሞክሩ!
ከመካከላችሁ አንድም ጠቢብ አላገኝም።
[11]ዕድሜዬ አለቀ፤ ዕቅዴም ከሸፈ፤
የልቤም ሐሳብ ከንቱ ሆነ።
[12]እነዚህ ሰዎች ሌሊቱን ወደ ቀን
ይለውጣሉ፤
ጨልሞም እያዩ፣ "ብርሃን ቀርቦአል"
ይላሉ።
[13]ተስፋ የማደርገው ቤት መቃብር* ብቻ
ከሆነ፣
መኝታዬንም በጨለማ ካነጠፍሁ፣
[14]መበስበስን፣ 'አንተ አባቴ ነህ፤
ትልንም፣ 'አንቺ እናቴ' ወይም 'እኅቴ
ነሽ' ካልሁ፣
[15]ታዲያ፣ የእኔ ተስፋ ወዴት ነው?
ተስፋዬን የሚያይልኝስ ማን ነው?
[16]ወደ ሞት* ደጅ ይወርዳልን?
አብረንስ ወደ ትቢያ እንሄዳለንን?"

17፥1 መዝ88፥3-4፤ 143፥4፤መክ12፥1-7፤ ኢሳ38፥12
17፥2 ኢዮ6፥14፤ 11፥3፤መዝ22፥7፤ 119፥51፥ኤር20፥7፤ ሰቆ3፥14
17፥3 መዝ35፥2፡ 27፤40፥17፤119፥122 ፤ምሳ6፥1፤ኢሳ38፥14
17፥4 ኢዮ12፥12
17፥5 ዘፀ22፥15፤ ኢዮ11፥20
17፥6 ቀኍ2፤ዘኍ 12፥14፤1ነገ9፥7፤ኢዮ 30፥9፤ኤር15፥4
17፥7 ኢዮ2፥12፤ 16፥8፡16
17፥8 ዘፀ4፥14
17፥9 1ሳሙ2፥4፤ 2ሳሙ22፥21፤ኢዮ9፥ 30፤መዝ84፥7፤ምሳ 4፥18
17፥10 ኢዮ12፥2
17፥11 ቁ15፤ኢዮ 7፥6፤ኢሳ38፥10
17፥12 ኢዮ5፥17- 26፤11፥17፤ኢሳ 50፥11
17፥13 2ሳሙ14፥ 14፤ኢዮ3፥13፤መዝ 88፥18፤139፥8
17፥14 ኢዮ4፥19፤ 7፥5፤13፥28፤30፥28፡ 30፤መዝ16፥10፤49፥9
17፥15 ኢዮ7፥6፤ መዝ31፥22፤ሰቆ3፥ 18፤ሕዝ37፥11
17፥16 ዘኁ2፥7፤ ኢዮ3፥19፤7፥9፤20፥ 11፤21፥26፤33፥28፤ መዝ9፥13፤30፥3፤ 107፥18፤ኢሳ38፥10፡ 17፤ዮና2፥6
18፥1 ኢዮ8፥1
18፥2 ኢዮ8፥2፤ 16፥3
18፥3 ኢዮ12፥7፤ መዝ73፥22
18፥4 ኢዮ13፥14፤ 14፥18፤16፥9
18፥5 ኢዮ5፥14፤ 12፥25፤21፥17፤24፥1 7፤35፥15፤38፥15፤ምሳ

## በልዳዶስ

18 ሹሐዊው በልዳዶስ እንዲህ ሲል
መለሰ፤
[2]"ይህን ንግግር የምትጨርሰው መቼ ነው?
እስኪ ልብ ግዛ፤ ከዚያ በኋላ
እንነጋገራለን።
[3]ለምን እንደ ከብት መንጋ እንቈጠራለን?
እንደ ደንቈሮስ ለምን ታየናለህ?
[4]አንተ በቍጣ የነደድህ እንደ ሆነ፣
ምድር ባዶዋን ትቀራለች?
ወይስ ዐለት ከሥፍራው ተነቅሎ
ይወሰዳል?
[5]"የክፉዎች መብራት ይጠፋል፤
የእሳቱም ነበልባል ድርግም ይላል።
[6]የድንኳኑ ብርሃን ይጨልማል፤
መብራቱም በላዩ ይጠፋል፤
[7]የርምጃው ብርታት ይደክማል፤
የገዛ ዕቅዱም ይጥለዋል።
[8]እግሩ በወጥመድ ይያዛል፤
በመረብም ይተበተባል።
[9]አሽክላ ተረከዙን ይይዘዋል፤
ወስፈንጥርም ያጣብቀዋል።
[10]በምድር ላይ የሸምበቆ ገመድ፣
በመንገዱም ላይ ወጥመድ በስውር
ይቀመጥለታል።
[11]ድንጋጤ በዙሪያው ያስፈራራዋል፤
ተከትሎም ያሳድደዋል።
[12]መቅሠፍት ሊውጠው ቀርቦአል፤
ጥፋትም የእርሱን ውድቀት
ይጠባበቃል።

13፥9፤20፥20፤24፥20፤ኤር25፥10፤ማቴ25፥8፤ዮሐ8፥12 18፥6 ኢዮ5፥14፤8፥22፤11፥17፤12፥25 18፥7 ኢዮ5፥13፤13፥26፤15፥6 18፥8 ኢዮ19፥6፤መዝ9፥15፤10፥9፤35፥7፤57፥6፤66፥11፤140፥5፤ ሰቆ1፥13፤ሚክ7፥2፤ዕን1፥15 18፥9 ኢዮ22፥10፤30፥12፤ምሳ5፥22፤ ኢሳ24፥18፤ኤር48፥44፤አሞ5፥19 18፥10 1ሳሙ28፥9፤መዝ 140፥5፤ምሳ7፥22፤ኢሳ51፥20 18፥11 ቍ14፡18፤ኢዮ6፥4፤15፥21፤ 20፥8፡25፤24፥17፤ መዝ31፥13፤55፥4፤88፥15፤ኢሳ22፥18፤28፥19፤ ኤር15፥8፤ሰቆ2፥22

*13 በዕብራይስጡ፣ ሲኦል ይላል
*16 በዕብራይስጡ፣ ሲኦል ይላል

17፥1 *መቃብርም ተዘጋጅቶልኛል፤* የቍ10-16 ማብ ይመ።

17፥3 *አንተ ተያዥ ሁነኝ፤* ኢዮብ ቅን መሆኑንና ለቅጣትም የሚያደርስ በደል እንደሌለበት እግዚአብሔር ያረጋግጥለት ዘንድ ይጠይቃል።

17፥4 *ልባቸውን፤* የሦስቱን ወዳጆቹን ማለት ነው።

*17፥5፤* ኢዮብ ወዳጆቹ ላቀረቡበት የሐሰት ክስ መልስ ለመስጠት የተጠቀመበት ምሳሌ ነው።

*17፥6-9፤* ኢዮብ እውን እንዲሆንለት የጠየቀውን ዋስትና ኣላገኘውም፤ ከዚህም የተነሣ የማንም መዘባበቻ እንዲሆን ያበቃው እግዚአብሔር እንደ ሆነ ይሰማዋል። የቍ 8-9 ቃና ምጸት ነው ከተባለ፣ "ቅኖች" እና "ንጹሓን" የሚለው አገላለጽ የሚመለከተው ወዳጆቹን ነው።

17፥6 *መተረቻ፤* 30፥9 ይመ። የተናቀና መዘባበቻ የሆነ ማለት ነው (ዘዳ 28፥37 ይመ)። *ፊቱ ላይ የሚተፋበት፤* 30፥10 ይመ።

17፥7 *መላ አካሌም እንደ ጥላ፤* የ2፥7 ማብ ይመ።

*17፥10-16፤* ኢዮብ ንስሓ ቢገባ ጨለማው ወደ ብርሃን እንደሚለወጥለት ሶፋር ተስፋ ይሰጠዋል (11፥17)። ኢዮብም ለማስገረም ሲል ይህንኑ ቃል መልሶ ይናገራል (ቍ 12-16)። የሚቀረው ተስፋ መቃብር ብቻ ነው (ቍ 1 ይመ)፤ ይህ ደግሞ እንደ ቀድሞ ቤቱ አይሆንለትም (ቍ 13-15)።

17፥13 *ቤት፤* መክ 12፥5 ይመ። *በጨለማ፤* 18፥18 ይመ፤ የሙታን ዓለም ማለት ነው (የ10፥21 ማብ ይመ)።

*17፥14፤* በመቃብር የሚጠበቀው የመበስበስና የትሎች ቤተ ሰብ መሆን ብቻ ነው።

17፥15 *የእኔ ተስፋ ወዴት ነው?* 14፥19 ይመ።

17፥16 *ወደ ሞት ደጅ፤* 38፥17፤ ማቴ 16፥18 ይመ። በመስጴጦምያም የጥናት ጽሑፎች መሠረት ወደ ሙታን ዓለም የሚሄድ ሁሉ ተከታታይ በሆኑ ሰባት በሮች ውስጥ ማለፍ አለበት። *ትቢያ፤* የ7፥21 ማብ ይመ።

*18፥1-4፤* በልዳዶስ የኢዮብን ስሜታዊ ምላሽ ከራስ ወዳድነት የተነሣ፣ ምክንያታዊም ያልሆነ አድርጎ ቈጠረው።

*18፥5-21፤* የክፉ ሰው ዕጣ ፈንታ ምን እንደሆነ የሚያሳይ ቅኔ ነው (8፥11-19፤ 15፥20-35 ይመ)። ጻድቅ ሰው በዚህ ዓለም መከራ ሲደርስበት፣ ክፉ ሰው ደግሞ አልፎለት በምቾት ሲኖር ይታያል የሚለውን የኢዮብን ግንዛቤ በልዳዶስ ካለመቀበሉም በላይ፣ ኢዮብ አመለካከቱን እንዲያስተካክል ይፈልጋል። ማንኛውም ክፉ ሰው የጁን ዋጋ በዚህ ምድር የሚያገኝ ስለ መሆኑ በልዳዶስ አፉን ሞልቶ ይናገራል።

18፥5 *የክፉዎች መብራት ይጠፋል፤* 21፥17 ይመ። በምሳ 13፥9 ላይ ተደግሞአል፤ በብርሃን ተምሳሌትነት የቀረበው ሕይወት በሕልውናው እንዲያከትም ሆነ።

[13]ደዌ ቈዳውን ይበላል፤
የሞት በኵርም ቅልጥሙን ይውጣል።
[14]ተማምኖ ከሚኖርበት ድንኳን ይነቀላል፤
ወደ ድንጋጤም ንጉሥ ይነዳል።
[15]ድንኳኑ በእሳት ይያያዛል፤[a]
በመኖሪያውም ላይ ዲን ይበተናል።
[16]ሥሩ ከታች ይደርቃል፤
ቅርንጫፉም ከላይ ይረግፋል።
[17]መታሰቢያው ከምድር ገጽ ይጠፋል፤
ስሙም በአገር አይነሣም።
[18]ከብርሃን ወደ ጨለማ ይጣላል፤
ከዓለምም ይወገዳል።
[19]በሕዝቡ መካከል ልጅ ወይም ዘር
አይኖረውም፤
በኖረበትም አገር ተተኪ አያገኝም።
[20]ባጋጠመው ሁኔታ የምዕራብ ሰዎች
ይደነግጣሉ፤
የምሥራቅም ሰዎች በፍርሀት ይዋጣሉ።
[21]በእርግጥ የክፉ ሰው መኖሪያ፣
እግዚአብሔርንም የማያውቅ ሰው መድረሻ
ይህ ነው።”

## ኢዮብ

19 ኢዮብም እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]“ነፍሴን የምታስጨንቋት፣
በቃልስ የምትደቍሱኝ እስከ መቼ ነው?
[3]እነሆ፤ ዐሥር ጊዜ ዘለፋችሁኝ፤
ያለ ዕፍረትም በደላችሁኝ።
[4]በእውነት ተሳስቼ ከሆነ፣
ስሕተቱ የራሴ ጕዳይ ነው።
[5]ነገር ግን ራሳችሁን በእኔ ላይ ከፍ
ብታደርጉ፣
መዋረዴንም እኔን ለመሞገት
ብትጠቀሙበት፣
[6]እግዚአብሔር እንደ በደለኝ፣
በመረቡም እንደ ከበበኝ ዕወቁ።

[7]“ ‘ተበደልሁ!’ ብዬ ብጮኽ ማንም
አይመልስልኝም፤
ድምፄን ከፍ አድርጌ ባሰማም፣ ፍትሕ
አላገኝም።
[8]እንዳላልፍ መንገዴን ዘግቶአል፤
መሄጃዬንም በጨለማ ጋርዶአል።
[9]ክብሬን ገፍፎኛል፤
ዘውዴንም ከራሴ ላይ ወስዶአል።
[10]እስክወገድ ድረስ በሁሉ አቅጣጫ
አፈራርሶኛል፤
ተስፋዬንም እንደ ዛፍ ነቅሎታል።
[11]ቍጣው በላዬ ነዶአል፤
እንደ ጠላቱም ቈጥሮኛል።
[12]ሰራዊቱ ገፍተው መጡ፤
በዙሪያዬ ምሽግ ሠሩ፤
ድንኳኔንም ከበው ሰፈሩ።
[13]“ወንድሞቼን ከእኔ አርቆአል፤
ከሚያውቁኝም ተገለልሁ።
[14]ዘመዶቼ ትተውኛል፤
ወዳጆቼም ረስተውኛል።
[15]የቤቴ እንግዶችና ሴት አገልጋዮቼ እንደ
መጻተኛ ቈጠሩኝ፤
እንደ ባዕድም ተመለከቱኝ፤
[16]አገልጋዬን ብጣራ፣
በአንደበቴም ብለምነው፣
አይመልስልኝም።
[17]እስትንፋሴ ለሚስቴ እንኳ የሚያስጠላት
ሆነ፤
የገዛ ወንድሞቼም ተጸየፉኝ።

18፥12 ኢዮ15፥23፤21፥17፤31፥3፤ኢሳ8፥21፤9፥20፤65፥13
18፥13 ዘኍ12፥12፤ዘካ14፥12
18፥14 ቍ11፤ኢዮ8፥22፤15፥24
18፥15 ቍ18፤ዘፍ19፥24፤ኢዮ20፥26
18፥16 ዘፍ27፥28፤ኢዮ8፥12፤15፥30፤ኢሳ5፥24፤ሆሴ5፥12፤አሞ2፥9
18፥17 ዘዳ9፥14፤32፥26፤ኢዮ24፥20፤መዝ9፥5፤34፥16፤69፥28፤ምሳ2፥22፤10፥7፤ኢሳ14፥22፤49፥15
18፥18 ቍ11፤ኢዮ5፥14፤11፥20፤30፥8
18፥19 2ነገ10፥11፤ኢዮ27፥14-15፤መዝ21፥10፤37፥28፤109፥13፤ኢሳ1፥4፤14፥20፡22፤ኤር22፥30፤ሕዝ17፥8
18፥20 መዝ22፥6-7፤37፥13፤ኢሳ52፥14፤53፥2-3፤ኤር46፥21፤50፥27፡31፤ሕዝ7፥7፤27፥35
18፥21 ኢዮ4፥21፤7፥10፤21፥28፤ኢሳ57፥20፤1ተሰ4፥5
19፥2 ኢዮ6፥9፤13፥25
19፥3 ዘፍ31፥7፤ኢዮ20፥3
19፥4 ኢዮ6፥24
19፥5 መዝ35፥26፤38፥16፤55፥12
19፥6 ኢዮ6፥29፤10፥3፤18፥8
19፥7 ኢዮ9፥24፤30፥20፡24፡28፤31፥35፤መዝ5፥2፤22፥2፤ዕን1፥2-4
19፥8 ኢዮ3፥26፤23፥17፤30፥26፤መክ6፥4፤ኢሳ59፥9፤ኤር8፥15፤14፥19፤ሰቆ3፥2፡7፤ሆሴ2፥6 19፥9 ዘፍ43፥28፤ዘፀ12፥42፤ኢዮ2፥8፤12፥17፤29፥14፤መዝ15፥4፤50፥23፤89፥39፡44፤ምሳ14፥31፤ሰቆ5፥16 19፥10 ኢዮ7፥6፤12፥14፤14፥7 19፥11 ኢዮ13፥24፤16፥9 19፥12 ኢዮ3፥23፤16፥10፡13 19፥13 ቍ19፤ኢዮ16፥7፤42፥11፤መዝ31፥11፤38፥11፤69፥8፤88፥8 19፥14 ቍ19፤2ሳሙ15፥12፤ኢዮ12፥4፤16፥20፤መዝ88፥18፤ኤር20፥10፤38፥22
19፥15 ዘፍ14፥14፤መክ2፥7 19፥17 መዝ38፥5

[a]15 *ወይም ምንም አይተርፍለትም ማለት ነው*

18፥13 *የሞት በኵርም፤* 5፥7 ይመ።

18፥14 … *ድንጋጤም ንጉሥ፤* ሞትን የሚያመለክት ዘይቤያዊ ገለጻ ነው፤ በቍ 13 ላይ በሰውኛ ዘይቤ ቀርቦአል። የከነዓናውያን ጥንታዊ ጽሑፍ ሁሉን በሚሰለቅጠው “ሞት” በተባለው ጣዖት አምላክ መስሎታል። ኢሳይያስ ደግሞ ይህን ተምሳሌት ለወጥ በማድረግ ጌታ ሞትን ለዘላለም እንደሚውጥ ገልጾአል (ኢሳ 25፥8፤ 1ቆሮ 15፥54 ይመ)።

18፥15 *ዲን፤* ሰዶምንና ገሞራን የሚያስታውስ ገለጻ ነው (ዘፍ 19፥24 ይመ)።

18፥16 *ሥሩ… ቅርንጫፉም፤* ከአሞ 2፥9 ጋር ያነጻጽሩ። ትውልድን (ኢሳ 11፥1፡10 ይመ) ወይም ቅድመ አያቶችን (መሳ 5፥14፤ ኢሳ 14፥29 ይመ) የሚያመለክት ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው።

18፥17 *መታሰቢያው… ይጠፋል፤* በልዳዶስ የሞት ቅጣት ምን እንደ ሆነ በትክክል አያውቅም፤ በእርሱ አስተሳሰብ ከሞት በኋላ ያለው ከፍተኛ ቅጣት ወራሽ ሳይተኩ ያለመታሰቢያ መቅረት ነው (ቍ 19 ይመ)።

18፥18 *ጨለማ፤* 17፥13 ይመ። የሙታን ዓለም ወይም ከምድር በታች ማለት ነው (የ10፥21 ማብ ይመ)።

18፥21 *የክፉ ሰው — እግዚአብሔርንም የማያውቅ፤* እግዚአብሔርን በጥልቀት አለማወቅና ክፉ ሰው ሆኖ መገኘት አንድ ናቸው (ሆሴ 4፥1-2፡6 ይመ)።

19፥3 *ዐሥር ጊዜ፤* አብዛኛውን ጊዜ ብዛትን ያመለክታል (ዘፍ 31፥41፤ 1ሳሙ 1፥8 ይመ)።

19፥4 *የራሴ ጕዳይ፤* የኢዮብ ወዳጆች በነገር ውስጥ ጣልቃ የመግባት ወይም እግዚአብሔር የሚያደርገውን የማከናወን መብትና ሥልጣን የላቸውም (ቍ 22 ይመ)።

19፥6 *በደለኝ፤* ከ40፥8 ጋር ያነጻጽሩ በ8፥3 ላይ በዕብራይስጥ ሁለት ጊዜ “ማዛነፍ” ተብሎ ተተርጕሞአል፤ በልዳዶስም እግዚአብሔር ፍርድን አያዛንፍም በማለት የተከራከረው በዚያ ስፍራ ላይ ነው። ነገር ግን ኢዮብ መከራን ለምን እንደሚቀበል ስላልተረዳ እግዚአብሔርን እንደ ጠላቱ ቈጥሮታል፤ እግዚአብሔር ግን በኢዮብ ደስ የተሰኘበት ወዳጁ ነበር (1፥8፤ 2፥3 ይመ)። እውነተኛ የኢዮብ ጠላት ግን ሰይጣን ነበር። *በመረቡም… ከበበኝ፤* በልዳዶስ እንዳመለከተው (18፥8-10) ክፉዎች በራሳቸው ላይ መከራ ሊያመጡ ይችላሉ፤ እዚህ ላይ ግን ኢዮብ መከራውን ከእግዚአብሔር ጋር ያያይዘዋል።

19፥7 *‘ተበደልሁ’ ብዬ ብጮኽ፤* በቍሙ ግፍ በመፈጸሙ ድምጽን ከፍ አድርጎ ማሰማት ማለት ነው (ዕን 1፥2 ይመ)።

*19፥8-12፤* በኢዮብ አስተሳሰብ ከእርሱ ጋር ጦርነት የገጠመው እግዚአብሔር ነው (16፥12-14 ይመ)።

19፥10 *ተስፋዬንም እንደ ዛፍ ነቅሎታል፤* 24፥20 ይመ፤ ይህም ኢዮብ በ14፥7-9 ላይ ከተቈረጠ በኋላ ተመልሶ የሚያቈጠቍጠውን ዛፍ የተስፋ ምልክት አድርጎ ከተጠቀመበት ዘይቤ ጋር የሚቃረን ነው።

19፥12 *ምሽግ፤* 30፥12 ይመ።

*19፥13-19፤* ኤር 12፥6 ይመ። በቤተ ሰብ ወይም በወዳጅ የመጠላትን ያህል አንድን ሰው የሚጐዳው ነገር የለም። የኢዮብ ልጆች አለቁበት፤ ሚስቱ፣ ወንድሞቹ፣ ወዳጆቹና አገልጋዮቹ ደግሞ ጠሉት።

19፥17 *እስትንፋሴ… የሚያስጠላት፤* የ2፥7 ማብ ይመ።

[18]ሕፃናት እንኳ ይንቁኛል፤
ባዩኝም ቍጥር ያላግጡብኛል።
[19]የቅርብ ወዳጆቼ ሁሉ ተጸየፉኝ፤
የምወዳቸውም በላዬ ተነሡ፤
[20]ቈዳና ዐጥንት ብቻ ሆኜ ቀረሁ፤
ድድ ብቻ ቀርቶልኝ አመለጥሁ።

[21]"ወዳጆቼ ሆይ፤ ራሩልኝ፤
የእግዚአብሔር እጅ መታኛለችና
ዕዘኑልኝ።
[22]እግዚአብሔር እንዳሳደደኝ ለምን
ታሳድዱኛላችሁ?
አሁንም ሥጋዬ አልበቃችሁምን?

[23]"ምነው ቃሌ በተጻፈ ኖሮ!
በመጽሐፍም በታተመ!
[24]ምነው በብረትና በእርሳስ በተጻፈ ኖሮ!
በዐለትም ላይ በተቀረጸ!
[25]የሚቤዠኝ ሕያው እንደ ሆነ፣
በመጨረሻም በምድር ላይ
እንደሚቆም ዐውቃለሁ።
[26]ቈዳዬ ቢጠፋም፣
ከሥጋዬ ብለይም፣ እግዚአብሔርን አየዋለሁ፤
[27]ሌላ ሳይሆን እኔው በገዛ ዐይኔ፣
እኔ ራሴ አየዋለሁ፤
ልቤ በውስጤ ምንኛ ዛለ!

[28]" 'የችግሩ መንሥኤ በውስጡ* አለ፤
እኛ እንዴት እናሳድደዋለን?' ብትሉ፣
[29]ቍጣ በሰይፍ መቀጣትን ያስከትላልና፣
ራሳችሁ ሰይፍን ፍሩ፤
በዚያን ጊዜ ፍርድ† እንዳለ
ታውቃላችሁ።"

19፥18 2ነገ2፥23፤ ኢዮ16፥10
19፥19 ቍ13፥14፤ ኢዮ6፥14፤30፥10፤ መዝ55፥12-13፤ ዮሐ13፥18
19፥20 ኢዮ2፥5
19፥21 መሳ2፥15፤ ኢዮ4፥5፤6፥14፤ 10፥3፤ሰቆ3፥1
19፥22 ቍ6፤2ዜና 8፥9፤ኢዮ13፥25፤መዝ 14፥4፤27፥2፤69፥26፤ ምሳ30፥14፤ኢሳ53፥4
19፥23 ዘፀ17፥14፤ መዝ40፥7፤ኢሳ8፥1
19፥24 ኢዮ16፥18፤ ኤር17፥1
19፥25 ዘፀ6፥6፤ዘሌ 25፥25፤1ሳሙ14፥39፤ ኢዮ16፥19፤መዝ68፥ 5፤78፥35፤ምሳ23፥11፤ ኢሳ41፥14፤43፥14፤ 44፥6፤24፤47፥4፤48፥ 17፤49፥26፤54፥5፤ 59፥20፤60፥16
19፥26 ዘኍ12፥8፤ ማቴ5፥8፤1ቆሮ13፥12 ፤1ዮሐ3፥2
19፥27 መዝ42፥1፤ 63፥1፤84፥2፤ሉቃ 2፥30
19፥28 ኢዮ13፥25
19፥29 ኢዮ15፥22፤ 27፥13-23፤መዝ1፥5፤ 9፥7፤58፥11፤መክ3፥ 17፤11፥9፤12፥14
20፥1 ኢዮ2፥11
20፥2 መዝ42፥5፤ ሰቆ1፥20
20፥3 ኢዮ19፥3
20፥4 ዘዳ4፥32፤ 32፥7
20፥5 ኢዮ8፥12፤ 13፤መዝ37፥35-36፤73፥19፤94፥3 20፥6 ዘፍ11፥4፤ኢዮ33፥17፤ኢሳ 14፥13-14፤16፥6፤አብ1፥3-4 20፥7 ኢዮ4፥20፤7፥8፤14፥20 20፥8 ኢዮ18፥11፤27፥20፤34፥20፤መዝ73፥20፤90፥5፤10፤መክ5፥3፤6፥12፤ 12፥7፤ኢሳ17፥14፤29፥7 20፥9 ኢዮ7፥8

## ሶፋር

# 20

ናዕማታዊውም ሶፋር እንዲህ ሲል መለሰ፤

[2]"እጅግ ታውኬአለሁና፣
ሐሳቤ መልስ እንድሰጥ ይጐተጕተኛል።
[3]የሚያቃልለኝን ንግግር ሰምቼአለሁ፤
መልስም እሰጥ ዘንድ መንፈሴ ገፋፋኝ።

[4]"ሰው* በምድር ላይ ከተቀመጠ ጊዜ
ጀምሮ፣
ከጥንቱ እንዴት እንደ ነበረ
ታውቃለህን?
[5]የኃጢአተኞች መፈንጨት ለአጭር ጊዜ፣
የክፉዎችም ደስታ ለቅጽበት መሆኑን
አታውቅምን?
[6]እስከ ሰማይ ከፍ ከፍ ቢልም፣
ዐናቱም ደመናትን ቢነካ፣
[7]እንደ ኵበት ለዘላለም ይጠፋል፤
ቀድሞ ያዩትም፣ 'የት ገባ?' ይላሉ።
[8]እንደ ሕልም በሮ ይጠፋል፤ አይገኝምም፤
እንደ ሌሊትም ራእይ በቅጽበት
ያልፋል።
[9]ቀድሞ ያየው ዐይን ዳግመኛ አያየውም፤
የነበረበትም ቦታ ከእንግዲህ
አይመለከተውም።

*28 አብዛኞቹ የዕብራይስጥ ቅጆች፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕምና ቩልጌት፣ *በእኔ* ይላሉ
†29 ወይም *ሁሉን ቻዩን ታውቃላችሁ* ማለት ነው
*4 ወይም *አዳም* ማለት ነው

19፥18 *ሕፃናት... ይንቁኛል፤* ሽማግሌዎች በከፍተኛ ሁኔታ በሚከበሩበት በጥንቱ ማኅበረ ሰብ ይህ ሊታገሡት የማይ ቻል ስድብ ነበር (ዘፀ 20፥12 እና ማብ ይመ)።

19፥20 *ቈዳና ዐጥንት፤* የ2፥7 ማብ ይመ። *ድድ፤* ጥርሱም እንኳ ሳይቀር መርገፉን ያመለክታል። በአማራጭነት የቀረበውን ትርጕም ይመ።

19፥21 *የእግዚአብሔር እጅ መታኛለችና፤* 1፥11፤ 2፥4-6፤ እንዲሁም የቍ 6 ማብ ይመ።

*19፥23-27፤* ኢዮብ ስለ ራሱ ሁኔታ፣ በእርሱና በእግዚአ ብሔር መካከል ስላለውም ግንኙነት በትክክል በመረዳት፣ ከፍ ተኛ ደረጃ ላይ የደረሰበት፣ በኢዮብ መጽሐፍ ካሉት ምንባቦች ሁሉ ዕውቁና ተወዳጁ ክፍል ነው። ይህም ክፍል፣ ኢዮብ ወዳጆ ቹን ተውኝ እባካችሁ ባለበትና (ቍ 21-22) በኋላም ለወዳጆቹ ማስጠንቀቂያ በሰጠበት (ቍ 28-29)፣ በእነዚህ ሁለት ክፍሎች መካከል በመገኘቱ ጎልቶ ሊታይ ችሎአል።

19፥23 *ቃሌ፤* ኢዮብ፣ ሰቆቃውና መከራከሪያ ሐሳቡ በጽ ሑፍ እንዲሰፍሩለት ይፈልጋል፤ ይኸውም እርሱ ከሞተ በኋላ ቋሚ ምስክር በመሆን የቱን ያህል ከበደል ነጻ እንደ ነበር እንዲ ያረጋግጡለት ነው። *በመጽሐፍም፤* የዘፀ 17፥14 ማብ ይመ።

19፥24 *በብረትና፤* 20፥24፤ 28፥2፤ 40፥18፤ 41፥27 ይመ። እስከ 12ኛው ዓ.ቅ.ክ. ድረስ ብረት አገልግሎት ላይ አል ዋለም ነበር።

19፥25 *የሚቤዠኝ ሕያው እንደ ሆነ—ዐውቃለሁ፤* ይህን ጽኑ የእምነት መግለጫ ክርስቲያኑ ትውልድ የራሱ አድርጎ ወስዶታል። በኢዮብ አእምሮ ውስጥ ያለው ከዚህ የተለየ ነበር። በሌላ ዐውድ ላይ የሚከላከልለት ቢፈልግም እንኳ (በአማራጭ የቀረበውን ትርጕም እንዲሁም ምሳ 23፥11 ይመ) በሰማይ ስለ እርሱ ከእግዚአብሔር ጋር የሚሟገትለት ጠበቃ ይፈልጋል (9፥33-34፤ 16፥18-21 እንዲሁም 5፥1 ማብ ይመ)። በዚህ ስፍራ የሚቤዠው ራሱ እግዚአብሔር እንጂ ሌላ አይደለም (የሩት 2፥20 ማብ ይመ)። ይህ ሁሉ የሐሰት ክስ በታማኝ አገልጋዮቹ ላይ ቢቀ ርብም እንኳ ዙሮ ዙሮ እግዚአብሔር ከበደል ነጻ እንደሚያደር ጋቸው ኢዮብ በጽኑ ያምናል። *በመጨረሻም፤* በቀሙ የኢዮብ ሕይ ወት ካለፈች በኋላ ማለት ነው። *እንደሚቆም፤* ሊከራከርልኝና ነጻ ሊያወጣኝ ማለት ነው።

19፥26 *ቈዳዬ ቢጠፋም፤* ኢዮብ የያዘው በሽታ በመጨረሻ ለሞት እንደሚያበቃው ያምናል። *እግዚአብሔርን አየዋለሁ፤* ሞት የሕይወት መደምደሚያ እንዳልሆነና አንድ ቀን በአዳኙ ፊት እንደሚቆም፣ በገዛ ዐይኑም ፊት ለፊት እንደሚያየው ኢዮብ ፍጹም እርግጠኛ በመሆን ይናገራል (ቍ 27፤ ማቴ 5፥8፤ 1ዮሐ 3፥2 ይመ)፤ የ42፥5 ማብ ይመ።

19፥28 *እናሳድደዋለን?* በቍ 22 ላይ ዕብራይስጡ፣ "መከታተል" ይለዋል። ከዋቂት ዕረፍት በኋላ (ቍ 23-27) የኢ ዮብ ቀጣ መቀጠሉን የሚያመለክት ቃል ነው።

*20፥1-29፤* "ከኛ ወዲያ ትክክለኛ ትምህርተ ሃይማኖት ለአሳር ነው" የሚሉት የኢዮብ ወዳጆች የክፉዎች ዕጣ ፈንታ ምን እንደሚመስል ያቀረቡት ሌላው ቅኔ ነው (8፥11-19፤ 15፥20-35፤ 18፥5-21 ይመ)።

*20፥2-3፤* ሶፋር የኢዮብን ቃል በተለይም በ19፥28-29 ላይ ያለውን መዝጊያ እንደ ስድብ ቈጥሮታል። በሌላም በኩል ሶፋር ባሰማው የቅጣት ደንብ መሠረት የጥፋቱ ተጠያቂ ወይም መቀ ጣት ያለበት ሶፋር ራሱ መሆን እንዳለበት ኢዮብ በልበ ሙሉ ነት ይናገራል።

*20፥4-11፤* ሶፋር በራሱ ግምት ባለሙሉ ጤናና ባለ ጸጋ በመሆኑ፣ ይህ ራሱ የመልካምነትና የጽድቅ ምልክት ነው በማ ለት ይከራከራል፤ የክፉዎች ደስታ ግን ምን ጊዜም ቅጽበታዊና እማይጨበጥ ነው (መዝ 73፥18-20 እና ማብ ይመ)።

20፥6 *እስከ ሰማይ ከፍ ከፍ ቢልም፤* ዘፍ 11፥4 እና ማብ ይመ።

20፥7 *ኵበት፤* የጊዜያዊነትና የከንቱነት ምልክት ነው (1ነገ 14፥10 ይመ)።

[10]ልጆቹ ለድኾች ካሣ መክፈል አለባቸው፤
እጆቹም ሀብቱን መልሰው መስጠት
ይገባቸዋል።
[11]ዐጥንቱን የሞላው የወጣትነት ብርታት፣
ከእርሱ ጋር በዐፈር ውስጥ ይተኛል።
[12]"ክፋት በአፉ ውስጥ ቢጣፍጥ፣
ከምላሱም በታች ቢደብቀው፣
[13]አውጥቶ ለመጣል እየሳሳ፣
በአፉ ውስጥ ቢያቈየው፣
[14]ምግቡ በሆዱ ውስጥ ይመራል፤
በውስጡም እንደ እባብ መርዝ ይሆናል።
[15]የዋጠውን ሀብት ይተፋል፤
እግዚአብሔርም መልሶ ከሆዱ ያወጣዋል።
[16]የእባብ መርዝ ይጠባል፤
የእፉኝትም ምላስ ይገድለዋል።
[17]ማርና ቅቤ በሚያፈሱ ጅረቶች፣
በወንዞችም አይደሰትም።
[18]የለፋበትን ሳይበላው ይመልሳል፤
ከንግዱም ባገኘው ትርፍ አይደሰትም፤
[19]ድኾችን በመጨቈን ባዶ
አስቀርቶአቸዋልና፣
ያልሠራውንም ቤት ነጥቆአል።
[20]"ክፉ ምኞቱ ዕረፍት አይሰጠውም
ሀብቱም ሊያድነው አይችልም።
[21]ያለውን አሟጦ ስለሚበላ፣
ዘላቂ ብልጽግና አይኖረውም።
[22]በተድላ መካከል እያለ ጒስቍልና
ይመጣበታል፤
በከባድ መከራም ይዋጣል።
[23]ሆዱን በሞላ ጊዜ፣
እግዚአብሔር የሚነድ ቍጣውን
ይሰድበታል፤
መዓቱንም ያወርድበታል።
[24]ከብረት መሣሪያ ቢሸሽም፣
የናስ ቀስት ይወጋዋል።
[25]ቀስቱን ከጀርባው፣
የሚያብለጨልጨውንም ጫፍ ከጒበቱ
ይመዛል፤
ፍርሀትም ይይዘዋል፤
[26]ሀብቱ ለድቅድቅ ጨለማ ተዳርጎአል፤
ሰው ባላራገበው እሳት ይበላል፤
በድንኳኑም ውስጥ የተረፈውን ይልሳል።
[27]ሰማያት ኀጢአቱን ይገልጡበታል፤
ምድርም ትነሣበታለች፤
[28]በእግዚአብሔር የቍጣ ቀን ቤቱን ጐርፍ፣
መኖሪያውንም ወራጅ ውሃ[^]
ይወስድበታል።
[29]እግዚአብሔር ለኀጢአተኞች የወሰነው ዕድል
ፈንታ፣
ከአምላክም ዘንድ የተመደበላቸው ቋሚ
ቅርስ ይህ ነው።"

20፥10. ቍ 15፡18፤ 20፤ኢዮ3፥15፤5፥4፤ 31፥8
20፥11 ኢዮ13፥26፤ 17፥16፤21፥24
20፥12 ኢዮ15፥16፤ መዝ10፥7፤140፥3
20፥13 ዘኍ11፥18-20
20፥14 ዘኍ21፥6፤ ምሳ 20፥17፤ኤር2፤ 19፥4፥18፤ራእ10፥9
20፥15 ቍ 10፤ ዘሌ18፥25
20፥16 ዘዳ32፥24፡32
20፥17 ዘዳ32፥13፡ 14፤ኢዮ29፥6፤ መዝ36፥8
20፥18 ቍ 10፤ኢዮ 5፥5፤መዝ109፥11
20፥19 ዘዳ15፥11፤ 24፥14፤ኢዮ5፥16፤ 24፥4፡14፡35፥9፤መዝ 10፥2፤94፥6፤109፥16 ፤ምሳ14፥31፤28፥28፤ ኢሳ5፥8፤አሞ8፥4
20፥20 ቍ 10፤ምሳ11፥4፤መክ 5፥12፤ሰፎ1፥18፤ሉቃ 12፥15
20፥21 ኢዮ7፥8
20፥22 ቍ 29፤መሳ 2፥15፤ኢዮ21፥17፡ 30፤31፥2-3፤ሉቃ 12፥16-20
20፥23 ቍ 14፤ዘኍ11፥18-20 ፤መዝ78፥30-31፤ሰቆ 4፥11፤ሕዝ5፥13፤6፥12
20፥24 ኢዮ15፥22፤ ኢሳ24፥18፤ኤር46፥ 21፤48፥44
20፥25 ኢዮ15፥21፤ 18፥11፤መዝ88፥15-16
20፥26 ኢዮ1፥16፤ 5፥14፤15፥34፤18፥15 ፤26፥6፤28፥22፤31፥ 12፤መዝ21፥9
20፥27 ዘዳ31፥28
20፥28 ቍ 29፤ዘኍ 14፥28-32፤ዘዳ28፥31 ፤ኢዮ21፥17፡20፡30፤ 40፥11፤

## ኢዮብ

# 21

[1]ኢዮብም እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"ቃሌን በጥንቃቄ ስሙ፤
የምታጽናኑኝም በዚህ ይሁን፤
[3]ንግግሬን በትዕግሥት አድምጡ፤
ከተናገርሁ በኋላ፣ መሣለቅ ትችላላችሁ።
[4]"በውኑ ቅርታዬ በሰው ላይ ነውን?
ትዕግሥት ማጣትስ አይገባኝምን?
[5]ተመልከቱኝና ተገረሙ፤
አፋችሁን በእጃችሁ ለጒሙ።
[6]ስለዚህ ነገር ባሰብሁ ቍጥር
እደነግጣለሁ፤
ሰውነቴም በፍርሀት ይንቀጠቀጣል።
[7]ኀጢአተኞች ለምን በሕይወት ይኖራሉ?
ለምን ለእርጅና ይበቃሉ? ለምንስ
እያየሉ ይሄዳሉ?

መዝ60፥3፤75፥8፤ምሳ16፥4፤ኢሳ24፥18፤51፥17፤አሞ5፥18፤ ማቴ7፥26-27፤ዮሐ3፥36፤ሮሜ1፥18፤ኤፌ5፥6 20፥29 ቍ 22፤ኢዮ 15፥20፤22፥5፤31፥2፤36፥17፤ኤር13፥25፤ራእ21፥8 21፥2 ቍ 34፤ ኢዮ13፥17 21፥3 ኢዮ6፥14፤11፥3፤16፥10 21፥4 ኢዮ6፥3፤ 7፥11 21፥5 መሳ18፥19 21፥6 ዘፍ45፥3፤ኢዮ4፥14 21፥7 ቍ 13፤ኢዮ9፥ 24፥12፥19፤መዝ37፥1፤73፥3፤መክ7፥15፤8፥14፤ዕን 1፥13፤ሚል3፥15

[^]28 ወይም *በቤቱ ውስጥ ያለውን ንብረት ወራጅ ውሃ ይወስድበታል ማለት ነው*

*20፥10፡19፤* ድኻን የሚጨቍን ሰው ክፋቱ የቱን ያህል እንደ ሆነ በትክክል ያመለክታል፤ (አሞ 2፥6-8፤ 8፥4-8 ይመ)። በዚህ ሐሳብ ላይ ኢዮብ ከሶፋር ጋር ምንም ተቃውሞ የለውም (31፥16-23 ይመ)።

20፥11 *በዐፈር፤* የ7፥21 ማብ ይመ።

*20፥12-15፤* የክፉ ሰው ክፋት በአፍ ውስጥ እንደሚጣፍጥ፣ በሆድ ውስጥ ግን እንደሚኾመጥጥ ምግብ ነው።

20፥15 *የዋጠውን ሀብት፤* የድሆችን ጥሪት ከሰበሰበ በኋላ ማለት ነው (የቍ 10፡19 ማብ ይመ)።

20፥18 *የለፋበትን... አይደሰትም፤* የቅኔ መጻሕፍት ዋና ሐሳብ ነው (መክ 2፥18-23 ይመ)።

*20፥20-25፤* ክፉ ሰው ሆዱ እስኪሞላ ድረስ ቢበላም እንኳ፣ እግዚአብሔር ቍጣውን ባፈሰሰበት ጊዜ ግን፣ የሚቀምሰው ነገር አይኖረውም።

20፥24 *ከብረት፤* የ19፥24 ማብ ይመ።

20፥26 *ጨለማ፤* የ10፥21 ማብ ይመ።

*20፥27፤* ዘዳ 30፥19 ማብ ይመ።

20፥28 *ጐርፍ —ወራጅ ውሃ፤* በክረምት ሞልቶ የሚፈስና ከፍተኛ ጒዳት የሚያስከትል ወራጅ ውሃ ነው (6፥15-16 ይመ)።

*20፥29፤* በልዳዶስ በ18፥21 ላይ እንደገለጸው ሶፋርም በበኩሉ እርሱ የተናገረው ሁሉ፣ እግዚአብሔር ኀጢአተኞችን ለመቅጣት ካሰበው ዕቅድ ጋር የሚስማማ መሆኑን በመግለጽ ሐሳቡን ይደመድማል። *እግዚአብሔር ለኀጢአተኞች የወሰነው ዕድል ፈንታ፤* በ27፥13 ላይ ኢዮብ በድጋሚ ይናገረዋል።

21፥2 *የምታጽናኑኝም፤* ቍ 34 ይመ።

21፥4 *በውኑ ቅርታዬ በሰው ላይ ነውን?* ኢዮብ እንዲህ ይላል "ሊሆን አይችልም፤ እኔ አቤቱታዬ ወደ እግዚአብሔር ነው፤ የደረሰብኝም መከራ ለምን እንደ ሆነ የሚያውቀው እርሱ ነውና"፤ ሌላው ቢቀር ኢዮብ የደረሰበትን ሥቃይ ያያዘው ከእግዚአብሔር ጋር ነው። *ትዕግሥት ማጣትስ፤* የ9፥2-3 ማብ ይመ።

21፥5 *ተመልከቱኝና፤* ኢዮብ ሦስቱ ወዳጆቹ ሁኔታውን በጥሞና እንዲያዩለት ያሳስባል።

21፥6 *ስለዚህ፤* አቤቱታውን የሚያቀርበው ወደ እግዚአብሔር ነው። *እደነግጣለሁ፤* ክፉዎች አምሮባቸውና አልፎላቸው የሚኖሩበት ሁኔታ በሥነ ምግባር ረገድ ሲታይ የተገላቢጦሽ የሆነበትን ጒዳይ ማለት ነው።

*21፥7-15፤* የኢዮብ ወዳጆች የክፉዎች ዕጣ ፈንታ ምን እንደሚሆን በሰፊው ያብራራሉ (8፥11-19፤ 15፥20-35፤ 18፥5-21፤ም 20 ይመ)፤ ኢዮብ ግን በገሀድ ያለው ነገር እነርሱ ካሉት የተለየ እንደ ሆነ አበክሮ ይናገራል፤ የእግዚአብሔርን መንገድ ለማወቅ የማይፈልጉና፣ ጸሎትንም ዋጋ቉ቢስ እንደ ሆነ የሚቈጥሩ (ቍ 14-15) ክፉዎች የሚያደርጉት ሁሉ ይሳካላቸዋል። ሶፋር እንዳሰበው ባጭሩ የሚቀጩ ሳይሆኑ (20፥11)፣ ረጅም ዕድሜ አላቸው፤ እየጠነከሩም በመሄድ ላይ ናቸው (ቍ 7)። ክፉዎች ዘርም ተተኪ ትውልድም አይወጣላቸውም (18፥19) የሚለውን የበልዳዶስን ሐሳብ ዳዊት ሳያወላውል ይቃወማል (ቍ 8፡11)።

8 ዘራቸው በዐይናቸው ፊት፣
ልጆቻቸውም በዙሪያቸው ጸንተው ሲኖሩ
ያያሉ፤
9 ቤታቸው ያለ ሥጋት በሰላም ይኖራል፤
የእግዚአብሔርም በትር የለባቸውም::
10 ኮርማቸው ዘሩ በከንቱ አይወድቅም፤
ያስረግዛል፤
ላማቸውም ሳትጨነግፍ ትወልዳለች::
11 ልጆቻቸውን እንደ በግ መንጋ ያሰማራሉ፤
ሕፃናታቸውም ይቦርቃሉ::
12 በከበሮና በክራር ይዘፍናሉ፤
በዋሽንትም ድምፅ ይፈነጫሉ::
13 ዕድሜያቸውን በተድላ ያሳልፋሉ፤
በሰላምም[ሀ] ወደ መቃብር[ለ] ይወርዳሉ::
14 እግዚአብሔርንም እንዲህ ይሉታል፤
‘አትድረስብን!
መንገድህንም ማወቅ አንፈልግም::
15 እናገለግለው ዘንድ፣ ሁሉን ቻይ አምላክ
ማን ነው?
ወደ እርሱ ብንጸልይስ ምን እናገኛለን?’
16 ይሁንና ብልጽግናቸው በእጃቸው አይደለም፤
ከኀጢአተኞች ምክር እርቃለሁ::

17 “የኀጢአተኞች መብራት የጠፋው ስንት
ጊዜ ነው?
የእግዚአብሔር ቍጣ መከራ የመጣባቸው፣
መቅሠፍትም የደረሰባቸው ስንት ጊዜ
ነው?
18 በነፋስ ፊት እንዳለ ገለባ፣
በዐውሎ ነፋስም እንደ ተወሰደ ዕብቅ
የሆኑት ስንት ጊዜ ነው?
19 እናንተ፣ ‘እግዚአብሔር የሰውን ቅጣት
ለልጆቹ ያከማቻል’ ትላላችሁ፤
ነገር ግን ያውቀው ዘንድ ለሰውየው
ለራሱ ይክፈለው፤
20 ዐይኖቹ የራሱን ውድቀት ይዩ፤
ሁሉን ከሚችል አምላክ ቍጣ ይጠጣ::
21 ሰው ወራቱ በተገባደደ ጊዜ፣
ለቀሪ ቤተ ሰቡ ምን ይገደዋል?

22 “ከፍ ባሉት ላይ ለሚፈርድ አምላክ፣
ዕውቀትን ሊያስተምረው የሚችል አለን?
23 አንድ ሰው በፍጹም ተድላ ደስታ
እየኖረ፣
በሙሉ ብርታቱም እያለ ይሞታል፤
24 ሰውነቱ[መ] በምቾት፣
ዐጥንቱም በስብ ተሞልቶ እያለ በሞት
ይለያል::
25 ሌላው ሰው ደግሞ አንዳች መልካም ነገር
ሳያይ፣
በተመረረች ነፍስ ይሞታል፤
26 ሁለቱም በዐፈር ውስጥ አንድ ላይ
ይተኛሉ፤
ትልም ይወርሳቸዋል::

27 “እነሆ፣ ምክራችሁን፣
በእኔ ላይ ያሜራችሁትንም
ተረድቻለሁ::
28 እናንተ፣ ‘የትልቁ ሰው ቤት፣
ኀጢአተኛውም የኖረበት ድንኳን የት
አለ?’ አላችሁ፤
29 መንገደኞችን አልጠየቃችሁምን?
የነገሯችሁንስ ነገር በጥሞና
አላዳመጣችሁምን?
30 ክፉ ሰው በመቅሠፍት ቀን
እንደሚጠበቅ፣
በቍጣም ቀን እንደሚተርፍ[ሠ]
አታውቁምን?
31 ተግባሩን ፊት ለፊት የሚነግረው ማን
ነው?
የእጁንስ ማን ይሰጠዋል?
32 ወደ መቃብር ይወስዱታል፤
ለመቃብሩም ጠባቂ ይደረግለታል::
33 የሸለቆው ዐፈር ምቹ ይሆንለታል፤
ሰው ሁሉ ይከተለዋል፤
ስፍር ቍጥር የሌለው ሕዝብ[ረ] በፊቱ
ይሄዳል::

34 “መልሳችሁ ከሐሰት በስተቀር ሌላ
አይገኝበትም፤
ታዲያ፣ በማይረባ ነገር እንዴት
ልታጽናኑኝ ትችላላችሁ!”

## ኤልፋዝ

**22** ቴማናዊውም ኤልፋዝ እንዲህ ሲል መለሰ፤

21፥8 መዝ17፥14፤ ሚል3፥15
21፥9 ኢዮ5፥24፤ 9፥34
21፥10 ዘፀ23፥26
21፥11 መዝ78፥52፤107፥41
21፥12 ዘፍ4፥21፤ 1ዜና15፥16፤መዝ33፥2፤71፥22፤81፥2፤ 108፥2፤ኢሳ5፥12፤ ማቴ11፥17
21፥13 ቍ7፤ኢዮ 3፥13፤8፥7፤24፥19፤ መዝ10፥1-12፤49፥ 14፤94፥3፤ኢሳ14፥15
21፥14 ዘጸ32፥15፤ 1ሳሙ15፥11፤ኢዮ4፥ 17፤22፥17፤መዝ95፥ 10፤ምሳ1፥29፤ኢሳ 30፥11፤ኤር2፥20:31
21፥15 ኢዮ5፥2፤ 34፥9፤35፥3፤መዝ 73፥13፤139፥20፤ኢሳ 48፥5፤ኤር9፥6፤44፥17
21፥16 ኢዮ22፥18፥ መዝ1፥1፤26፥5፤36፥1
21፥17 ኢዮ18፥5: 12፤20፥22:28
21፥18 ዘፍ7፥23፤ 19፥15፤ኢዮ7፥10፤ 13፥25፤ምሳ10፥25
21፥19 ዘፀ20፥5፤ ኤር25፥14፤31፥29፤ 50፥29፤51፥6:24:56፤ ሕዝ18፥2፤ዮሐ9፥2
21፥20 ዘፀ32፥33፤ ዘኍ16፥22፤2ነገ14፥6 ፤ኢዮ6፥4፤20፥28፤ ኤር25፥15፤42፥16፤ ራእ14፥10
21፥21 ኢዮ14፥5: 21:22፤መክ9፥5-6
21፥22 ኢዮ4፥18፤ 35፥11፤36፥22፤39፥ 17፤መዝ82፥1፤86፥8፤ 94፥12፤135፥5፤ኢሳ 40፥13-14፤ኤር32፥ 33፤ሮሜ11፥34
21፥23 ዘፍ15፥15፤ ኢዮ3፥13፤13፥26
21፥24 ኢዮ20፥11፤ መዝ73፥4፤ምሳ3፥8
21፥25 ኢዮ10፥1
21፥26 ኢዮ7፥5፤ 17፥16፤24፥20፤መክ 9፥2-3፤ኢሳ14፥11
21፥28 ኢዮ1፥3፤ 8፥22፤12፥21፤29፥ 25፤31፥37
21፥30 ኢዮ20፥22: 28፤31፥3፤ኢሳ5፥30፤ ሮሜ2፥5፤2ጴጥ2፥9
21፥31ኢዮ34፥11፤መዝ62፥12፤ምሳ24፥11-12፥ኢሳ59፥18
21፥32 ኢሳ14፥18 21፥33 ኢዮ3፥19:22 21፥34 ቍ2፤ኢዮ 6፥15፤8፥20 22፥1 ኢዮ4፥1

[ሀ]13 በዕብራይስጡ፣ ሲኦል ይላል
[ለ]13 ወይም በፍጥነት ማለት ነው
[ሐ]17-20፤ ቍ 17:18 ቃለ አጋኖዎች ሲሆኑ ቍ 19:20 ደግሞ ብያኔዎች ናቸው::
[መ]24 የዚህ ቃል የዕብራይስጡ ትርጕም በትክክል አይታወቅም
[ሠ]30 ወይም ለመቅሠፍት ቀን ተጠብቆ እንደሚቈይ ማለት ነው
[ረ]33 ወይም ስፍር ቍጥር እንደ ሌለው ሕዝብ ማለት ነው

21፥9 *የእግዚአብሔርም በትር፤* የ9፥34 ማብ ይመ::

21፥13 *በሰላምም፤* በዕብራይስጥ ሥርወ ቃሉ በመዝ 35፥20 ላይ፣ “በጸጥታ የሚኖሩ” ተብሎ ተተርጕሞአል::

*21፥16፤* 22፥18 ይመ:: ኢዮብ የክፉዎችን ጠማማ ምክር የማይበጅ ነው በማለት ይቃወማል፤ እግዚአብሔር ሁሉንም ነገር እንደሚቈጣጠር ያውቃል (ቍ 17)፤ ይህ ግንዛቤው ግን የመለኮት ባሕርይ የባሰውን ምስጢር እንዲሆን አድርጎበታል::

21፥17 *የኀጢአተኞች መብራት የጠፋው፤* 18፥5 ማብ ይመ::

21፥18 *ገለባ... ዕብቅ፤* 13፥25 እና የመዝ 1፥4 ማብ ይመ::

21፥20 *ሁሉን ከሚችል አምላክ ቍጣ ይጠጣ፤* የኢሳ 51፥17 ማብ ይመ::

21፥22 *አምላክ፣ ዕውቀትን ሊያስተምረው የሚችል አለን?* ኢሳ 40፥14 ይመ:: የሚያስተምረው ግን ሌላ ሳይሆን እግዚአብሔር ነው (35፥11፤ 36፥22፤ ም 38-41 ይመ)::

21፥26 *በዐፈር፤* የ7፥21 ማብ ይመ::

21፥34 *እንዴት ልታጽናኑኝ ትችላላችሁ?* 16፥2 እና ማብ ይመ::

*22፥1-26፥14፤* ይህ የሦስተኛው ዙር ውይይት እንደ መጀመሪያውና (ም 4-14) እንደ ሁለተኛው(ም 15-21)፣ በጣም ረጅም ሳይሆን፣ አጥር ምጥን ብሎ የቀረበ ነው፤ በልዳዶስ ንግግሩን በአጭሩ አቅርቦአል (25፥1-6)፤ ሶፋርም አንዳች ነገር አልተናገረም:: የኢዮብ ወዳጆች፣ አንተ በደለኛ ነህ በማለት ሊያሳምኑት ባለመቻላቸው፣ በሁለቱ መካከል ያለው ክርክር ከዚህ ላይ ያከትማል፤ ኢዮብ በበኩሉ እውነት ያልሆነውን ነገር አምኖ መቀበል አልቻለም::

²"ሰው እግዚአብሔርን ሊጠቅም ይችላልን?
ጠቢብ እንኳ ቢሆን ምን ይጠቅመዋል?
³አንተ ጻድቅ ብትሆን ሁሉን የሚችለውን
አምላክ ምን ደስ ታሰኘዋለህ?
መንገድህ ያለ ነቀፋ ቢሆንስ
የሚተርፈው ምንድን ነው?

⁴"እርሱ የሚገሥጽህ፣
ፍርድ ቤትም የሚያቀርብህ
ስለምትፈራው ነውን?
⁵ክፋትህ ታላቅ፣
ኀጢአትህ ፍጻሜ የሌለው አይደለምን?
⁶ያለ አንዳች ምክንያት ከወንድሞችህ
መያዣ ወስደሃል፤
ሰዎችን ገፈህ፣ ያለ ልብስ
ዕራቍታቸውን አስቀርተሃል።
⁷የዛሉትን ውሃ አላጠጣህም፤
የተራቡትንም ምግብ ከልክለሃል።
⁸ባለ ርስትና ኀያል፣
በእርሱም የምትኖር ክቡር ሰው ብትሆንም፣
⁹መበለቶችን ባዶ እጃቸውን ሰደሃል፤
የድኻ ዐደጎችንም ክንድ ሰብረሃል።
¹⁰ድንገተኛ አደጋ ያናወጠህ፤
ወጥመድም ዙሪያህን የከበበህ ለዚህ ነው።
¹¹እንዳታይ ጨለማ የሆነብህ፣
ጐርፍም ያጥለቀለቀህ ለዚህ ነው።

¹²"እግዚአብሔር ከፍ ባለው ሰማይ የሚኖር
አይደለምን?
በሩቅ ከፍታ ያሉትን ከዋክብት ያያል!
¹³ይህም ሆኖ ሳለ እንዲህ አልህ፤ 'እግዚአብሔር
ምን ያውቃል?
በእንዲህ ያለ ጨለማ ውስጥስ ይፈርዳልን?
¹⁴በሰማይ ክበብ ላይ ሲራመድ፣
እንዳያየን ጥቅጥቅ ያለ ደመና ይሸፍነዋል።'
¹⁵ኀጢአተኞች በሄዱባት፣
በጥንቷ መንገድ እንደ ተመላለስህ
ትቀራለህን?
¹⁶ጊዜያቸው ሳይደርስ ተነጠቁ፤
መሠረታቸውም በጐርፍ ተወሰደ።
¹⁷እግዚአብሔርንም 'አትድረስብን!
ሁሉን የሚችል አምላክም ምን
ያደርግልናል?' አሉ።
¹⁸ቤታቸውን በመልካም ነገር የሞላው ግን
እርሱ ነው፤
ስለዚህ ከኀጢአተኞች ምክር እርቃለሁ።
¹⁹"ጻድቃንም የእነዚያን ጥፋት አይተው
ይደሰታሉ፤
ንጹሓንም እንዲህ ብለው ያፌዙባቸዋል፤
²⁰'በእርግጥ ጠላቶቻችን ጠፍተዋል፤
ሀብታቸውም በእሳት ተበልቶአል።'

²¹"ከእግዚአብሔር ተገዛ፤ ከእርሱም ጋር ሰላም
ይኑርህ፤
በረከትም ታገኛለህ።
²²ምክርን ከአፉ ተቀበል፤
ቃሉንም በልብህ አኑር።
²³ሁሉን ወደሚችል አምላክ ብትመለስ
ትጠገናለህ፤
ክፋትን ከድንኳንህ ብታርቅ፣
²⁴የወርቅህን አንኳር ትቢያ ላይ፣
የኦፊር ወርቅህንም ጥልቅ ሸለቆ ውስጥ
ብትጥለው፣

22፥2 ኢዮ7፥17፤ ሉቃ17፥10
22፥3 ኢዮ35፥7፤ መዝ143፥2፤ምሳ9፥12፤ኢሳ1፥11፤ሐጌ1፥8
22፥4 ኢዮ9፥3፤19፥29፤መዝ143፥2፤ ኢሳ3፥14፤ሕዝ20፥35
22፥5 ዕዝ9፥13፤ኢዮ15፥5፡13፤20፥29፤29፥17
22፥6 ዘፀ22፥26፡27፤ዘዳ24፥12-13፤ 2ነገ4፥1
22፥7 ቍ9፤ኢዮ29፥12፤31፥17፡21፡31፤ ኢሳ58፥7፡10፤ሕዝ18፥7፤ ማቴ10፥42፤25፥42
22፥8 ኢዮ12፥19፤15፥19፤ኢሳ3፥3፤5፥13፤9፥15
22፥9 ቍ7፤ኢዮ6፥27፤24፥3፡21፤29፥13፤31፥16፤መዝ146፥9፤ ኢሳ1፥17፤10፥2፤ ሉቃ1፥53
22፥10 ኢዮ10፥3፤15፥21፤18፥9
22፥11 ዘፍ7፥23፤ ኢዮ5፥14፤36፥28፤38፥34፡37፤መዝ69፥1-2፤124፥4-5፤ኢሳ58፥10-11፤ሰቆ3፥54
22፥12 ኢዮ11፥8፤16፥19
22፥13 ቍ14፤መዝ10፥11፤59፥7፤64፥5፤73፥11፤94፥7፤139፥11፤ኢሳ29፥15፤ሕዝ8፥12፤9፥9፤ሰፎ1፥2፤ ኤፌ6፥12
22፥14 ቍ13፤2ነገ21፥16፤ኢዮ26፥9፤37፥18፤መዝ18፥11፤97፥2፤105፥39፤ምሳ8፥27፤ኢሳ40፥22፤ ኤር23፥23-24
22፥15 ኢዮ23፥10፤34፥8፡36፤መዝ1፥1፤50፥18 22፥16 ዘፍ7፥23፤ኢዮ4፥19፤15፥32፤ማቴ7፥26-27 22፥17 ኢዮ21፥15 22፥18 ኢዮ12፥6፤21፥16 22፥19 ኢዮ21፥3፤መዝ5፥11፤9፥2፤32፥11፤52፥6፤58፥10፤64፥10፤97፥12፤107፥42 22፥20 ኢዮ15፥30፤መዝ18፥39 22፥21 ዘፍ17፥1፤ኢዮ8፥7፤መዝ34፥8-10፤ምሳ3፥10፤ኢሳ26፥3፡12፤27፥5፤ኤር9፥24፤ሮሜ5፥1፤1ጴጥ5፥6 22፥22 ዘዳ8፥3፤ኢዮ6፥10፤15፥11፤28፥23፤መዝ37፥31፤40፥8፤ምሳ2፥6፤ሕዝ3፥10 22፥23 ኢዮ5፥24፤11፥14፤ኢሳ19፥22፤31፥6፤44፥22፤55፥7፤59፥20፤ኤር3፥14፡22፤ሕዝ18፥32፤ዘካ1፥3፤ሚል3፥7፤ሐሥ20፥32 22፥24 ዘፍ10፥29፤ኢዮ1፥10፤28፥6፤31፥25፤መዝ19፥10፤ኢሳ2፥20፤30፥22፤31፥7፤40፥19-20፤ማቴ6፥19

*22፥2-4፤* የኤልፋዝ አጕል አመለካከት እንደሚከተለው ነው፤ ሁሉም ነገር ከእግዚአብሔር የመነጨ በመሆኑ፣ ሰው እግዚአብሔር የሰጠውን መልሶ ለባለቤቱ መስጠቱ ለመለኮት ሞገስ አይጨምርለትም። ሰው በጎ ይሠራ ዘንድ ከእርሱ የሚጠበቅ በመሆኑም፣ እግዚአብሔር ስለ ሰው በጎ ሥራ አይገደውም። እግዚአብሔርን የሚገደው ግን ሰው ክፉ ሆኖ ሲገኝ ብቻ ነው (ቍ 4)።

22፥4 *ስለምትፈራው፤* የ4፥6 ማብ ይመ። *ፍርድ ቤትም የሚያቀርብህ፤* የ9፥3 ማብ ይመ።

*22፥5-11፤* የኤልፋዝ የመጀመሪያ ንግግር የሚጎንጥ ዐይነት ሳይሆን፣ ይልቁንም የቀረበው እንደ አጽናኝ ሰው ሆኖ ነበር (4፥6፤ 5፥17)፤ ይሁን እንጂ በ4፥3-4 ላይ ይህን የመሰለ ሐሳብ ቢያቀርብም እንኳ፣ በማኅበራዊ ተግባር ረገድ የተላለፍከው ነገር አለ በማለት ኢዮብን ይወቅሰዋል፤ ይኸውም የተራቈቱትንና የተቸገሩትን (ቍ 6-7)፣ መበለቶችንና አባት አልባ የሆኑትን (ቍ 9) በድለሃል የሚል ነው። ይሁን እንጂ ኢዮብ ፈጽሞአል ለተባለው በደል ኤልፋዝ ማስረጃ አድርጎ ያቀረበው በዚሁ ጊዜ በኢዮብ ላይ የደረሰውን ሥቃይ ብቻ ነው (ቍ 10-11)። በም 29 ላይ ኤልፋዝ ተላልፈሃል ያለውንም፣ ኢዮብ በብርቱ ቃል ይቃወማል።

22፥6 *መያዣ ወስደሃል... ያለ ልብስ ዕራቍታቸውን፤* እንዲህ ያለውን በደል ነቢያት አውግዘውታል (አሞ 2፥8 ማብ ይመ)።

22፥9 *መበለቶችን... የድኻ ዐደጎችንም፤* 24፥3፤ ኢሳ 1፥17 እና ማብ፤ ያዕ 1፥27 ይመ። *ክንድ፤* በቁሙ "እጅ" ማለት ነው (38፥15 ይመ)።

22፥10 *ወጥመድም፤* 19፥6 ማብ ይመ።

22፥11 *ጨለማ... ጐርፍም፤* የተለመዱ የመከራና የሐዘን መግለጫዎች ናቸው (መዝ 42፥7 እና ማብ፤ ኢሳ 8፥7-8፡22፤ 43፥2 ይመ)።

*22፥12-20፤* በመጨረሻም ኤልፋዝ፣ ኢዮብ ያለጥርጥር ክፉ ሰው ነው በማለት ከልብ የሚከራከሩትን የበልዳዶስንና የሶፋርን ክርክር ይደግፋል፤ በመሆኑም ኤልፋዝ ብርቱ ክስ ያቀርባል፤ ኢዮብ የክፉዎችን መንገድ በመከተል (ቍ 15)፣ ይኸውም የእግዚአብሔርን ኀይል የሚንቁትንና፣ "ሁሉን የሚችል አምላክ ምን ያደርግልናል?" (ቍ 17) የሚሉትን (ቍ 13-14 ይመ)፣ አልፈው ተርፈውም የእግዚአብሔርን ቸርነት የሚያቃልሉትን (ቍ 18) ወገኖች ሐሳብ ይከተላል በማለት ይቃወመዋል።

*22፥18፤* 21፥16 እና ማብ ይመ።

*22፥21-30፤* ኤልፋዝ ኢዮብን ለማሳመን በብዙ መንገድ የንስሓ ጥሪ በማቅረብ አንድ የመጨረሻ ሙከራ ያደርጋል፤ ወደ እግዚአብሔር ተመለስ (ቍ 21)፤ የእግዚአብሔርን ቃል በልብህ አኑር (ቍ 22)፤ ክፋትን ትተህ ሁሉን ወደሚችል ጌታ ዘወር በል (ቍ 23)፤ ከወርቅ ይልቅ በእግዚአብሔር ደስ ይበልህ (ቍ 24-26)፤ በጸሎት በርታ፤ ለእግዚአብሔርም ታዘዝ (ቍ 27)፤ ስለ ኀጢአተኞችም ሸክም ይኑርህ (ቍ 29-30) ይለዋል። ይህ የኤልፋዝ ምክር ግን 1) ኢዮብ ኀጢአተኛ መሆኑን፣ 2) ኢዮብ የቀድሞ ሀብቱ እንዲመለስለት የሚፈልግ መሆኑን (ቍ 21) የሚያመለክት ነው፤ ይሁን እንጂ ኢዮብ በ19፥25-27 ላይ እግዚአብሔርን ለማየትና የእርሱም ወዳጅ ለመሆን እንደሚናፍቅ ግልጽ አድርጎታል።

*22፥22፤* በ23፥12 ላይ የኢዮብን ምላሽ ይመ። *ቃሉንም በልብህ አኑር፤* መዝ 119፥11 ይመ።

22፥24 *የኦፊር ወርቅ፤* 28፥16 ይመ፤ ምርጥ የሆነ የወርቅ ዐይነት ነው (የ1ነገ 9፥28፤ የ10፥11፤ የመዝ 45፥9፤ የኢሳ 13፥12 ማብ ይመ)።

[25]ሁሉን ቻዩ አምላክ ወርቅ ይሆንልሃል፤
ምርጥ ብር ይሆንልሃል።
[26]በዚያ ጊዜ ሁሉን በሚችል አምላክ ደስ ይልሃል፤
ፊትህንም ወደ እግዚአብሔር ታቀናለህ።
[27]ወደ እርሱ ትጸልያለህ፤ እርሱም ይሰማሃል፤
አንተም ስእለትህን ትሰጣለህ።
[28]ያሰብኸው ይከናወንልሃል፤
በመንገድህም ላይ ብርሃን ይበራል።
[29]ሰዎች ቢዋረዱና አንተ፣ 'ከፍ አድርጋቸው' ብትል፣
እርሱ ዝቅ ያሉትን ያድናል፤
[30]በኀ ያልሆነውን ሰው እንኳ፣
ከአንተ እጅ ንጽሕና የተነሣ ያድነዋል።"

**ኢዮብ**

# 23

ኢዮብም እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"ዛሬም ሐዘኔ መራራ ነው፤
እያቃሰትሁ እንኳ እጁ* በላዬ ከብዳለች።
[3]እርሱን የት እንደማገኘው ባወቅሁ፤
ወደ መኖሪያውም መሄድ በቻልሁ!
[4]ጉዳዬን በፊቱ አቀርብ ነበር፤
አፌንም በሙግት እሞላው ነበር።
[5]የሚመልስልኝ ቃል ምን እንደ ሆነ ባወቅሁ ነበር፤
የሚለኝንም ባስተዋልሁ ነበር።
[6]በታላቅ ኀይሉ ከእኔ ጋር ይሟገት ይሆን?
አይደለም፤ ይልቁን ያደምጠኛል።
[7]ቅን ሰው ጉዳዩን በእርሱ ፊት ያቀርባል፤
እኔም ከፈራጄ ለዘላለም ነጻ እሆናለሁ።
[8]"ዳሩ ግን ወደ ምሥራቅ ብሄድ፣ በዚያ የለም፤
ወደ ምዕራብም ብሄድ፣ እርሱን አላገኘውም፤
[9]በሰሜን እየሠራ ሳለ አላየውም፤
ወደ ደቡብ በሚዞርበት ጊዜ ደብዛው አይገኝም።
[10]ግን እኔ የምሄድበትን መንገድ ያውቃል፤
ከፈተነኝም በኋላ እንደ ወርቅ እወጣለሁ።
[11]እግሮቼ እርምጃውን በጥብቅ ተከታትለዋል፤
ፈቀቅ ሳልል መንገዱን ጠብቄአለሁ።
[12]ከአፉ ከወጣው ትእዛዝ አልራቅሁም፣
የአንደበቱን ቃል ከዕለት እንጀራዬ አብልጬ ይዣለሁ።
[13]"እርሱ ግን ራሱን ችሎ ብቻውን የሚኖር ነው፤
የሚቃቃመውስ ማን ነው?
እርሱ የፈቀደውን ያደርጋል።
[14]በእኔ ላይ የወሰነውን ይፈጽማል፤
ይህን የመሰለ ዕቅድም ገና ብዙ አለው።
[15]በፊቱ የደነገጥሁትም ለዚህ ነው፤
ይህን ሁሉ ሳስብ እፈራለሁ።
[16]እግዚአብሔር ልቤን አባባው፤
ሁሉንም የሚችል አምላክ አስደነገጠኝ።
[17]ይህም ሆኖ ሳለ ጨለማው፣
ፊቴንም የጋረደው ጽልመት ልሳኔን አልዘጋውም።

# 24

"ሁሉን የሚችል አምላክ ለምን የፍርድ ቀን አይወስንም?

22፥25 2ነገ18፥7፤ ኢዮ31፥24፤መዝ49፥6፤52፥7፤ምሳ11፥28፤ ኢሳ33፥6፤ማቴ6፥20-21 22፥26 ኢዮ11፥15፡17፤27፥10፤33፥26፤ መዝ2፥8፤16፥6፤27፥6፤37፥4፤100፥1፤ኢሳ58፥14፤61፥10 22፥27 ዘኍ30፥2፤ ኢዮ5፥15፡27፤መዝ86፥7፤ኢሳ30፥19 22፥28 ኢዮ11፥17፤33፥28፤መዝ97፥11፤103፥11፤145፥19፤ ምሳ4፥18 22፥29 ኢሳ5፥12፤ መዝ18፥27፤ ማቴ23፥12 22፥30 2ሳሙ22፥21፤ኢሳ1፥18፤ሮሜ4፥5 23፥2 1ሳሙ1፥10፤ ኢዮ6፥3፤7፥11፤መዝ6፥6፤32፥4፤ኤር45፥3፤ ሕዝ21፥7 23፥3 ዘዳ4፥29 23፥4 ኢዮ9፥15፤13፥18 23፥5 ኢዮ11፥5 23፥6 ኢዮ6፥4፤9፥4 23፥7 ዘፍ3፥8፤ኢዮ1፥1፤6፥29፤9፥3፤13፥3 23፥9 ኢዮ9፥11 23፥10 ኢዮ1፥1፤6፥29፤7፥18፤22፥15፤27፥6፤31፥6፤36፥7፤ መዝ7፥9፤11፥5፤12፥6፤34፥15፤37፥18፤94፥11፤119፥168፤139፥1-3፤146፥8፤1ጴጥ1፥7 23፥11 ኢዮ31፥7፤ መዝ17፥5፤40፥4፤44፥18፤119፥51፡59፡157፤125፥5፤ኤር11፥20 23፥12 ኢዮ6፥10፤15፥11፤ማቴ4፥4፤ ዮሐ4፥32፡34 23፥13 ኢዮ9፥3፤10፥13፤ኢሳ55፥11 23፥14 1ተሰ3፥3፤1ጴጥ4፥12 23፥15 ዘፍ45፥3፤ኢሱ24፥14፤መዝ34፥9፤36፥1፤111፥10፤ምሳ1፥7፤መክ3፥14፤12፥13፤2ቆሮ5፥11 23፥16 ዘፀ3፥6፤ ዘዳ20፥3፤ኢዮ27፥2፤ራእ6፥16 23፥17 ኢዮ3፥6፤ 19፥8

*2 በሰብዓ ሊቃናት ትርጒም፣ በሱርስትና በዕብራይስጡ ላይ፣ እጅ በላዬ ይላል

22፥28 *በመንገድህም ላይ ብርሃን ይበራል፤* የእግዚአብሔርን ቃል በመታዘዝ የሚገኝ በረከት ነው (ቍ 22፥27፤ 29፥3፤ መዝ 119፥105 ይመ)።

22፥30 *ከአንተ እጅ ንጽሕና የተነሣ፤* የመዝ 24፥4 ማብ ይመ።

23፥2 *ሐዘኔ፤* 21፥4 ማብ ይመ። *እጁ በላዬ ከብዳለች፤* እጁ በእኔ ላይ ሆኖብኛል ማለት ነው፤ 33፥7 እና የ1ሳሙ 5፥6 ማብ ይመ።

23፥3 *እርሱን የት እንደማገኘው፤* የቍ 8-9 ማብ ይመ።

23፥6 *አይደለም፤ ይልቁን ያደምጠኛል፤* ኢዮብ ትክክለኛ ፍትሕ ማግኘት ይፈልጋል፤ በ9፥14-20 ላይ ኢዮብ ከእግዚአብሔር ጋር ለመከራከር ቃል እንደሚያጥረው በፍርሀት ገልጾአል። አሁን ግን እግዚአብሔር በቸርነቱ ቢሰማው፣ ከደረሰበት ሥቃይ እንደ ሚላቀቅ እርግጠኛ ነው (13፥13-19፤ እንዲሁም መዝ 17፥1-3፤ 26፥1-3 ማብ ይመ)።

23፥8-9 *ምሥራቅ... ምዕራብም... ሰሜን... ደቡብ፤* ኢዮብ በየትኛውም አቅጣጫ ቢሄድ እግዚአብሔርን ሊያገኝ አልቻለም (ከመዝ 139፥7-10 ጋር ያነጻጽሩ)።

23፥8፡10 *እርሱን አላገኘውም... ግን... የምሄድበትን መንገድ ያውቃል፤* ኢዮብ፣ ቅን መሆኑን በሚያውቅለት በእግዚአብሔር ዘንድ ተስሚነት በማጣቱ ተጨንቆአል። እዚህ ላይ ኢዮብ በ22፥21 ላይ "ለእግዚአብሔር ተገዛ... በረከትም ታገኛለህ" በማለት ኤልፋዝ ለሰጠው ማስጠንቀቂያ ምላሽ ይሰጣል፤ ይህንማ ዘወትር ይፈጽም እንደ ነበር ኢዮብ ይገልጻል (ቍ 11-12)፤ ከዕለት እንጀራው ይልቅ ለእግዚአብሔር ቃል ይጠነቀቃል። እግዚአብሔር ኢዮብን የሚፈትነው ከኀጢአቱ ሊያነጻው አስቦ ሳይሆን፣ ኢዮብ የነጠረ ወርቅ መሆኑን ለማሳየት እንደ ሆነ ኢዮብ ያምናል (መዝ 119፥11፡101፡168፤ 1ጴጥ 1፥7 ይመ)።

*23፥12፤* ኤልፋዝ ለሰጠው ምክር የኢዮብ ምላሽ በ22፥2 ላይ ተመልክቶአል። *ቃል ከዕለት እንጀራዬ አብልጬ፤* ዘዳ 8፥3 ይመ።

23፥13 *እርሱ... ብቻውን የሚኖር ነው፤* በቁሙ፣ "እርሱ ልዩ ነው" ማለት ነው፤ ኢዮብ እስራኤላዊ ባይሆንም እንኳ እውነተኛውንና ብቸኛውን አምላክ ያመልካል (ዘዳ 6፥4 ማብ ይመ)። *እርሱ የፈቀደውን ያደርጋል፤* እርሱ ልዑል ስለሆነ ነው (መዝ 115፥3፤ 135፥6 ሉቃ 10፥21 ይመ)።

23፥15 *የደነገጥሁትም፤* የ21፥6 ማብ ይመ። ዐይነተኛ የሆነው የኢዮብ እምነት የፈቀደውን ማድረግ የሚችለውን እግዚአብሔርን መፍራት ነው፤ በአንጻሩ ደግሞ መካሪዎቹ ጌታ ምን እንደሚሠራ አስቀድሞ ማወቅ ይቻላል ባዮች ናቸው።

23፥17 *ጽልመት ልሳኔን አልዘጋውም፤* ኢዮብ በ22፥11 ላይ ኤልፋዝ ላቀረበበት ክስ (ማብ ይመ) ምላሽ ይሰጣል።

*24፥1-12፤* ኢዮብ በምድር ላይ ተደጋግሞ ስለሚፈጸመው አሠቃቂ የፍትሕ መጓደል ይገልጻል። ለኢዮብ ባለ ጸጋውንም (ቍ 2) ሆነ ድኻውን (ቍ 3-4) መዘረፍ በተመሳሳይ ደረጃ ይዘ ገንኖአል። ነገር ግን በእርሱ ላይ የደረሰው መከራ፣ ምግብ ፍለጋ የሚንከራተቱትንና (ቍ 5) "ከክፉዎች የወይን በታም የሚቃርሙትን" (ቍ 6) ድኾች ችግር በአጽንዖት ለመግለጽ ሳይረዳው አልቀረም። ኢዮብ የሚያቀርበው መግለጫ የሚያሳቅቅ ነው፤ ድኾች በሌሊት ዕራቁታቸውን በብርድ ይሠቃያሉ (ቍ 7-8)፤ "አባት የሌላቸው ልጆች ከዕቅፍ ይነጠቃሉ" (ቍ 9)፤ "ነዶ ይሸከማሉ ግን ይራባሉ" (ቍ 10)፤ "ወይን እየጨመቁ... ይጠማሉ" (ቍ 11)፤ የቈሰሉት፣ በሞት አፋፍ ላይ ያሉትም ከሥቃይ የተነሣ ይጮኻሉ (ቍ12)። ይህ ዐይነቱ ሥቃይ ደርሶ ሳለ እግዚአብሔር

እርሱን የሚያውቁትስ ለምን ያን ቀን
 እንዲያው ይጠባበቃሉ?
[2]ሰዎች ድንበር ይገፋሉ፤
 የሰረቁትን መንጋ ያሰማራሉ።
[3]የድኻ ዐደጉን አህያ ቀምተው ይሄዳሉ፤
 የመበለቲቱንም በሬ በመያዣነት
 ይወስዳሉ።
[4]ችግረኛውን ከመንገድ ያስወግዳሉ፤
 የምድሪቱም ድኾች ይሸሸጋሉ።
[5]በምድረ በዳ እንዳሉ የሜዳ አህዮች፣
 ድኾች ምግብ ፍለጋ ይራወጣሉ፤
 ከበረሓው ምድር ለልጆቻቸው ምግብ
 ይሻሉ።
[6]ከሜዳ መኖ ይሰበስባሉ፤
 ከክፉዎች የወይን ቦታም ይቃርማሉ።
[7]ዕራቍታቸውን ያለ ልብስ ያድራሉ፤
 በብርድም ጊዜ የሚለብሱት የላቸውም።
[8]ከተራራ በሚወርድ ዝናብ በሰብሰዋል፤
 መጠለያ አጥተው ቋጥኝ ዐቅፈዋል።
[9]አባት የሌለው ልጅ ከዕቅፍ ተነጥቋል፤
 የድኻውም ልጅ በዕዳ ተይዞአል።
[10]ዕራቍታቸውን ያለ ልብስ ይሄዳሉ፤
 ነዶ ይሸከማሉ፤ ግን ይራባሉ።
[11]በየተረተሩ[*] የወይራ ዘይት ያወጣሉ፤
 ወይን እየጠመቁ፣ ለራሳቸው ግን ይጠማሉ፤
[12]የሚሞቱ ሰዎች ጣር ጩኸት ከከተማዋ ይሰማል፤
 የቈሰሉት ሰዎች ነፍስ ለርዳታ ይጮኻል፤
 እግዚአብሔር ግን ተጠያቂዎቹን ዝም
 ብሎአል።

[13]"በብርሃን ላይ የሚያምፁ፣
 ጐዳናውን የማያውቁ፣
 በመንገዱም የማይጸኑ አሉ።
[14]ቀኑ ሲመሽ፣ ነፍሰ ገዳይ ይነሣል፤
 ድኾችንና ችግረኞችን ይገድላል፤
 በሌሊትም እንደ ሌባ ያደባል፤
[15]አመንዝራ በዐይኑ ድንግዝግዝታን
 ይጠባበቃል፤
 'ማንም አያየኝም' ብሎ ያስባል፤
 ፊቱንም ይሸፍናል።
[16]በጨለማ፣ ቤት ሰርስረው ይገባሉ፤
 በቀን ግን ይሸሸጋሉ፤
 ብርሃንንም አይፈልጉም።
[17]ድቅድቅ ጨለማ ለሁሉም እንደ ንጋት[*]
 ነው፤
 አሸባሪውን ጨለማ[*] ይወዳጃሉ።
[18]"ይሁን እንጂ፣ በውሃ ላይ
 የሚኰረፈረፍ ዐረፋ ናቸው፤
 የወይን ቦታው ሰው የማይደርስበት፣
 ርስታቸው ርጉም ነው።
[19]ድርቅና ሙቀት የቀለጠውን በረዶ
 ከቦታው እንደሚያስወግድ፣
 ሲኦልም[*] ኀጢአተኞችን ትነጥቃለች።
[20]የተሸከመቻቸው ማሕፀን ትረሳቸዋለች፤
 ትል ይቦጠቡጣቸዋል፤
 ክፉዎች እንደ ዛፍ ይሰበራሉ፤
 የሚያስታውሳቸውም የለም።
[21]የማትወልደውን መካኒቱን ይቦጠቡጣሉ፤
 ለመበለቲቱም አይራሩም።
[22]ነገር ግን እግዚአብሔር ብርቱዎችን
 በኀይሉ ጐትቶ ይጥላል፤
 ቢደላደሉም የሕይወት ዋስትና
 የላቸውም።
[23]ያለ ሥጋት እንዲኖሩ ትቶአቸው
 ይሆናል፤
 ዐይኖቹ ግን በመንገዳቸው ላይ ናቸው።
[24]ለጥቂት ጊዜ ከፍ ከፍ ይላሉ፤ ሆኖም
 ይጠፋሉ፤
 ዝቅ ዝቅ ብለው፣ እንደ ሌሎቹ
 ይከማቻሉ።
 እንደ እሆል ራስም ይታጨዳሉ።
[25]"ይህ እንዲህ ካልሆነማ፣ የሚያስተባብለኝ
 ማን ነው?
 ቃሌን ከንቱ የሚያደርገውስ ማን ነው?"

24፥1 ኢዮ9፥23፤ 14፥5፤15፥20፤ሐሥ 1፥7፤2ጴጥ3፥7
24፥2 ዘዐ20፥15፤ ዘዳ19፥14፤28፥31
24፥3 ኢዮ6፥27፤ 22፥9
24፥4 ኢዮ20፥19፤ 29፥12፡16፤30፥25፤ 31፥19፤መዝ12፥5፤ 41፥1፤82፥3፡4፤ምሳ 28፥12፤ኢሳ11፥4
24፥5 ዘፍ16፥12፤ኢዮ30፥3፤መዝ104፤23
24፥6 ቍ18፤ሩት 2፥22፤1ነገ21፥19፤ ኢዮ6፥5
24፥7 ዘዐ22፥27
24፥8 መሳ6፥2፤ ሰቆ4፥5፤ዳን4፥25፡33
24፥9 ዘሌ25፥47፤ዘዳ24፥17፤2ነገ4፥1፤ኢዮ 29፥17፤መዝ14፥4፤ ምሳ30፥14፤ኢሳ3፥14 ፤10፥1-2፤ሕዝ18፥12
24፥10 ዘሌ19፥9፤ ዘዳ24፥12-13
24፥11 ኢሳ5፥2፤ 16፥10፤ሚክ6፥15፤ ሐጌ2፥16
24፥12 ኢዮ9፥23፤ 12፥19፤30፥28፤መዝ 5፥2፤22፥24፤39፥12፤ 119፥147፤ኢሳ30፥ 19፤ኤር50፥46፤51፥ 52፡54፤ሕዝ26፥15፤ ራእ6፥10
24፥13 ቍ16፤ኢዮ 17፥12፤38፥15፡20፤ መዝ18፥28፤ኢሳ5፥20 ፤ዮሐ3፥19-20፤ኤፌ 5፥8-14፤1ተሰ5፥4-5
24፥14 ኢዮ20፥19፤ መዝ10፥9፤37፥32፤ ኢሳ3፥15፤ሚክ3፥3
24፥15 ኢዮ31፥9፡ 27፤መዝ10፥11፤ምሳ 1፥10፤7፥8-9
24፥16 ቍ13፤ዘፀ 22፥2፤ማቴ6፥19
24፥17 ኢዮ15፥22፤ 18፥5፡11
24፥18 ቍ6፤ኢዮ5፥ 3፤9፥26፤22፥16፤ኢሳ 57፥20፤ይሁ1፥13
24፥19 ኢዮ6፥17፤ 21፥13 24፥20 ኢዮ7፥5፤14፥7፤18፥17፤21፥26፤መዝ31፥12፤ዳን 4፥14 24፥21 ኢዮ22፥9 24፥22 ዘዳ28፥66፤ኢዮ9፥4፤12፥19፤ ማቴ6፥27፤ያዕ4፥14 24፥23 2ዜና16፥9፤ኢዮ9፥24፤10፥4፤አሞ6፥1 24፥24 2ነገ19፥35፤ኢዮ3፥19፤4፥20፤መዝ37፥10፤83፥13፤ኢሳ5፥ 24፤17፥5፡13፤40፥24፤41፥2፡15 24፥25 ኢዮ6፥28፤16፥17

[*]11 ወይም *ከወፍጮዎች መካከል የወይራ ዘይት* ማለት ነው፤ ሆኖም የዚህ ቃል የዕብራይስጡ ትርጕም በትክክል አይታወቅም
[*]17 ወይም *ለእነርሱ ንጋት እንደ ሞት ጥላ ነው*
[*]17 ወይም *ከሞት ጥላ* ማለት ነው
[*]19 አንዳንድ ቅጆች፣ *መቃብር* ይሉታል

ለምን ዝም እንደሚል (ቍ 1፡12)፣ ለኢዮብ ምስጢር ነው፤ እግዚአብሔር ሰው እንደሚያስበው ሳይሆን፣ የራሱን ጊዜ ጠብቆ ሥራውን ማከናወኑ ግን፣ የኢዮብ ወዳጆች ትክክል ይሆናል በማለት ስለ ሥቃይ የሰነዘሩትን መሪ ሐሳብ ውድቅ ያደርገዋል። ኢዮብ ግን በቍ13-17 ላይ ሥቃይ እንደ ደረሰባቸው ምስኪኖች፣ ወይም ሥቃይ እንዳደረሱት ሰዎች፣ የእግዚአብሔር ጥበቃና ፍቅር የተለየው ሰው አይደለም።

*24፥1፤* የቍ 21-14 ማብ ይመ።

24፥2 *ድንበር ይገፋሉ፤* ድንበር መግፋት በጥንት ጊዜ ከፍተኛ ወንጀል ነበር (የዘዳ 19፥14 ማብ ይመ)።

24፥3 *የድኻ አደጉን... የመበለቲቱን፤* 22፥9፤ ኢሳ 1፥17 እና ማብ ያዕ 1፥27 ይመ።

24፥5 *የሜዳ አህዮች፤* 39፥5-8 ይመ።

24፥6 *ይቃርማሉ፤* የሩት 1፥22 ማብ ይመ።

*24፥7፡10፤* ኢዮብ በደፈናው የኤልፋዝን ክስ ይቃወማል (22፥6 ይመ)።

*24፥13-17፤* በቍ 2-12 ላይ ማንነታቸው እንደሚከተለው ተገልጾአል፤ እነርሱም ነፍሰ ገዳዮች (ቍ 14)፣ አመንዝራዎች (ቍ 15)፣ *ዘራፊዎች* (ቍ 16) ናቸው። የሚመላለሱትና ሕልውናቸውን የሚጠብቁት በጨለማ ነው (ቍ 14-17)፤ በሌላም በኩል ዐመፀኛ ሆነው የቆሙት ብርሃን በሆነው በእግዚአብሔር ሕግ ላይ ነው (ቍ 13፣ እንዲሁም የ22፥28 ማብ ይመ)።

*24፥18-20፤* ከዚህ ላይ ኢዮብ ከመካሪዎቹ ጋር የተስማማ ይመስላል። በሌላም በኩል ክፉ አድራጊዎች የእጃቸውን ያገኙ ዘንድ በእነዚህ ጥቅሶች አማካይነት ኢዮብ ጥሪ ያቀርባል ብሎ መተርጐምም ይቻላል፤ ለዚህ ሐሳብ መነሻ የሚሆኑትም የሚከተሉት ናቸው፤ "ርስታቸው ርጉም ነው፤... ሲኦልም ኀጢአተኞችን ትነጥቃለች፤ ... ማሕፀን ትረሳቸዋለች፤ ... ትል ይቦጠቡጣቸዋል፤ ክፉዎች እንደ ዛፍ ይሰበራሉ፤ የሚያስታውሳቸውም የለም።"

24፥20 *ትል ይቦጠቡጣቸዋል፤* 21፥26፤ ኢሳ 14፥11 ይመ። *እንደ ዛፍ ይሰበራሉ፤* የ19፥10 ማብ ይመ።

*24፥21-24፤* ኢዮብ በማጠቃለያው እግዚአብሔር በክፉዎች ላይ እንደሚፈርድ፣ ይህንንም የሚያደርገው በራሱ ጊዜ እንደ ሆነ ይናገራል። ይህንንም ቀን ጻድቃን ማየት ይችሉ ዘንድ እግዚአብሔር እንዲረዳቸው ኢዮብ ይመኛል (ቍ 1)።

24፥24 *እንደ እሆል ራስም ይታጨዳሉ፤* የፍርድ ምልክት ነው (የኢሳ 17፥5 ማብ ይመ)።

### በልዳዶስ

**25** ሹሐዊውም በልዳዶስ እንዲህ ሲል መለሰ፤

[2]"ገዢነትና ግርማ የእግዚአብሔር ናቸው፤
በሰማይም ከፍታ ሥርዐትን ያደርጋል።
[3]ሰራዊቱ ሊቈጠር ይችላልን?
ብርሃኑስ የማይወጣው በማን ላይ ነው?
[4]ሰው በእግዚአብሔር ፊት ጻድቅ ይሆን ዘንድ፣
ከሴትስ የተወለደ ንጹሕ ይሆን ዘንድ ይችላልን?
[5]በፊቱ ጨረቃ እንኳ ብሩህ ካልሆነች፣
ከዋክብትም ንጹሓን ካልሆኑ፣
[6]ይልቁን ከብል የሚቈጠር የሰው ልጅ፣
ትል የሆነውማ ሰው ምንኛ ያንስ!"

### ኢዮብ

**26** ኢዮብም እንዲህ ሲል መለሰ፤
[2]"ኀይል የሌለውን ምንኛ ረዳኸው!
ደካማውንስ ምንኛ አዳንኸው!
[3]ጥበብ የሌለውን ምንኛ መከርኸው!
ታላቅ ዕውቀትንስ ምንኛ ገለጥህለት!
[4]ይህን ቃል እንድትናገር የረዳህ ማን ነው?
የማንስ መንፈስ በአንደበትህ ተጠቀመ?
[5] "ከውሆችና በውስጣቸው ከሚኖሩ በታች ያሉ፣
የሙታን መንፈስ በጭንቅ ላይ ናቸው።
[6]ሲኦል' በእግዚአብሔር ፊት ዕራቍቷን ናት፤
የጥፋትንም˥ ስፍራ የሚጋርድ የለም።
[7]የሰሜንን ሰማይ በሕዋው ላይ ዘረጋው፤
ምድርንም እንዲያው በባዶው ላይ አንጠለጠላት።
[8]ውሆችን በደመናዎቹ ይጠቀልላል፤
ክብደታቸውም ደመናዎቹን አይሸነቍርም።
[9]ደመናዎቹን በላዩ ዘርግቶ፣
የሙሉውን ጨረቃ ፊት ይጋርዳል።
[10]ለብርሃንና ለጨለማ ድንበር ይሆን ዘንድ፣
በውሆች ላይ የአድማስ ክበብ አበጀ።
[11]የሰማይ ምሰሶዎች ይንቀጠቀጣሉ፤
በተግሣጹም ይደነግጣሉ።
[12]በኀይሉ ባሕርን ያናውጣል፤
በጥበቡም ረዓብን ይቈራርጣል።
[13]በእስትንፋሱ ሰማያትን አጠራ፤
እጁም ተወርዋሪውን እባብ ወጋች።
[14]እነዚህ የሥራው ዳር ዳር ናቸው፤
ስለ እርሱ የሰማነው ምንኛ አነስተኛ ነው!
የኀይሉንስ ነጐድጓድ ማን ሊያስተውል ይችላል?"

**27** ኢዮብም እንዲህ ሲል ንግግሩን ቀጠለ፤
[2]"ፍትሕ የነሣኝ ሕያው እግዚአብሔርን!
ነፍሴንም መራራ ያደረጋት፣ ሁሉን ቻይ አምላክን!

25፥1 ኢዮ8፥1
25፥2 2ዜና20፥6፤ ኢዮ9፥4፤11፥8፤16፥19፤መዝ47፥9፤89፥18፤ዘካ9፥7፤ራእ1፥6
25፥3 ማቴ5፥45፤ ያዕ1፥17
25፥4 ኢዮ4፥17
25፥5 ኢዮ4፥18፤ 31፥26
25፥6 ኢዮ4፥19፤ 7፥5፤መዝ80፥17፤ 144፥3፤ሕዝ2፥1
26፥2 ኢዮ4፥3፤ 6፥12
26፥3 ኢዮ34፥35
26፥4 1ነገ22፥24
26፥5 መዝ88፥10፤ ኢሳ14፥9፤26፥14
26፥6 ኢዮ10፥22፤ 11፥8፤20፥26፤38፥17፤41፥11፤መዝ139፥8፡ 11-12፤ምሳ15፥11፤ ዕብ4፥13፤ራእ9፥11
26፥7 ኢዮ9፥8፤38፥6፤መዝ104፥5፤ምሳ3፥19-20፤8፥27፤ኢሳ 40፥22
26፥8 ዘፍ1፥2፤ኢዮ 36፥27፤37፥11፤መዝ 147፥8፤ምሳ30፥4
26፥9 2ሳሙ22፥10፤ኢዮ22፥14
26፥10 ዘፍ1፥4፤ ኢዮ28፥3፤38፥8-11፤ ምሳ8፥27፤ኢሳ40፥22
26፥11 2ሳሙ22፥8
26፥12 ዘፀ14፥21፤ ኢዮ9፥13፤12፥13
26፥13 ኢዮ9፥8፤ ኢሳ27፥1
26፥14 ኢዮ4፥12፤ 9፥6፤42፥5፤ዕን3፥2፤1ቆሮ13፥12
27፥1 ኢዮ29፥1
27፥2 1ሳሙ1፥10፤ኢዮ6፥29፤7፥19፤9፥24፤10፥1፤23፥16፤49፥4፡14፤ኢሳ45፥9

'6 የዕብራይስጡ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ አንዳንድ ቅጆች ግን፣ ሞት ይላሉ።
˥6 ዕብራይስጡ፣ አባዶን ይላል።

*25፥1-6፤* የ22፥1-26፥4 ማብ ይመ። እዚህ ላይ በልዳዶስ ምንም አዲስ ነገር አልተናገረም፤ በሁኔታው ገራ ተጋብቶ በስሜት መናገሩን ያመኳጨው (20፥2 ይመ) ሶፋር ግን ምንም አስተ ያየት አልሰጠም።

25፥2 *በሰማይም ከፍታ ሥርዐትን ያደርጋል፤* በልዳዶስ መንግሥተ ሰማያት የጦርነት ቦታ እንደ ሆነ በመቍጠር፣ ሥርዐት ይሰፍንም ዘንድ እግዚአብሔር የሰማይ ሰራዊትን እንደሚያሰማራ ያምናል (ቍ 3 ይመ)።

25፥3 *ሰራዊቱ፤* የእግዚአብሔር መላእክት ናቸው። *ብርሃኑ፤* ፀሐይ ናት፤ በእግዚአብሔር ሥልጣን ሥር ያለው ሁሉ በእርሱ ፊት መጠውለጉ አይቀርም።

*25፥4-6፤* ኤልፋዝ ስለ ሰው ምግባረ ብልሹነት አስቀድሞ የተናገረውን ሐሳብ (4፥17-19፤ 15፥14-16)፣ በልዳዶስ እዚህ ላይ ይደገመዋል።

*26፥2-4፤* ኢዮብ ጠንከር ባለ ምጸት ለበልዳዶስ ይመልሳል፤ ኤልፋዝና ሶፋር ግን አፋቸውን እንዲይዙ ተደርገዋል።

26፥2 *ደካማውንስ... አዳንኸው፤* 4፥3-4፤ ኢሳ 35፥3፤ ዕብ 12፥12 ይመ።

*26፥5-14፤* ይህ የኢዮብ ቅኔ የእግዚአብሔር ኀይል ምን ያህል ታላቅ እንደሆነ የሚያሳይ ሲሆን፣ የበልዳዶስ የመደምደሚያ ንግግር ዐቢይ ሐሳብ ነው (ም 25)፣ ቅኔውም ውብ ተደርጐ የተጻፈ፣ በተምሳሌታዊ ገለጻዎችም የተሞላ ነው።

26፥5 *የሙታን፤* የዚህ ቃል የዕብራይስጥ ትርጕም በምሳ 2፥18 ላይ "የሙታን መናፍስት"፣ በኢሳ 14፥9 ላይ "በሞት የተለዩ ሰዎች መናፍስት" እንዲሁም በኢሳ 26፥14 "የሞቱት መናፍስት" ተብሎአል። እዚህ ላይ ኢዮብ በምሳሌያዊ ንግግሩ በሙታን ዓለም ያሉትን የመልእክት ማስተላለፊያ ያደርጋል (3፥13-15፡17-19 እንዲሁም የ3፥16 ማብ ይመ)። *ከውሆችና፤* ከሙታን ዓለም በላይ የሆነ፣ ሕይወት ያላቸው ነገሮች የሚኖሩበት የዓለም ክፍል ነው።

26፥6 *ሲኦል፤* በሌላ ቦታ "የድንጋጤ ንጉሥ" ተብሎአል (18፥14 እና ማብ ይመ)። *የጥፋትንም፤* በዕብራይስጥ "አብዶን" ይባላል፤ እንዲሁም 28፥22፤ 31፥21፤ ምሳ 15፥11 ይመ። በራእ 9፥11 ላይ አብዶን "የጥልቅ መላአክ" ስም ነው። በዕብራይስጥ አብዶን፣ በግሪክ አጰሊዮን ማለት አጥፊ ማለት ነው።

26፥7 *ዘረጋው፤* እግዚአብሔር ነው። *የሰሜንን ሰማይ... ዘረጋው፤* 37፥18 ይመ። *በሕዋው ላይ፤* በዘፍ 1፥2 በዕብራይስጡ "ቅርጽ አልባ" ተተርጕሞአል። *በባዶው ላይ፤* የ9፥6 ማብ ይመ።

26፥11 *የሰማይ ምሰሶዎች፤* የ9፥6 ማብ ይመ።

26፥12 *ባሕርን ያናውጣል፤* ኢሳ 51፥15፤ ኤር 31፥35 ይመ። *ረዓብ፤* የ9፥13 ማብ ይመ።

26፥13 *ተወርዋሪውን እባብ፤* የባሕር አውሬ የሆነው የሌዋታን ምንነት መግለጫ ነው (የ3፥8፤ የኢሳ 27፥1 ማብ ይመ)።

26፥14 *እነዚህ የሥራው ዳር ዳር ናቸው፤* እግዚአብሔር በተፈጥሮና በዲበ ተፈጥሮ ላይ የበላይነቱ (ገዢነቱ) ምን ያህል እንደ ሆነ የገለጠው የኢምንት ያህል ነው። ኢዮብ የሰው ማስተዋል እጅግ ውሱን በመሆኑ፣ በጣም ተደንቆአል። በሌላም በኩል ኢዮብ የእግዚአብሔርን ምስጢር ለማስተዋል ባለ መቻሉ (11፥7-9)፣ ሶፋር ገሥጾታል፤ ወዳጆቹ አለን ብለው የሚኵራሩበት ዕውቀት ግን ከኢዮብ ዕውቀት የላቀ አይደለም (12፥3፤ 13፥2 ይመ)። *የኀይሉንስ ነጐድጓድ፤* ስለ እግዚአብሔር ኢምንት ያህል የምናውቀውን ማስተዋል ካልቻልን፣ ሙሉ ኀይሉን የማስተዋል ጕዳይማ የቱን ያህል አስቸጋሪ ነው።

*27፥1-23፤* የመጽሐፉ የክርክር ክፍል የሚጀምረው፣ በኢዮብ የሰቆቃ መግቢያ ነው (ም 3)፤ ቀጥሎም በሦስት ዙር ንግግር በመጀመር (ም 4-14፤ 15-21፤ 22-26) ከበደል ነጻ መሆኑን በተናገረበት (ቍ 2-6)፣ በንግግሩ መደምደሚያ ያጠቃልለዋል (ም 27)፤ እንዲሁም በጥሩ አንደበት የክፉዎች የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ ምን እንደሚሆን ይገልጻል።

27፥2 *ሕያው እግዚአብሔርን፤* ይህ ጠንከር ያለ የመሐላ ቃል ነው (የዘፍ 42፥15 ማብ ይመ)። ኢዮብ፣ ፍትሕ ተንድሎብኛል ብሎ ቢያስብም እንኳ በእግዚአብሔር ላይ ያለው እምነት ጠንካራ ነው።

3በውስጤ የሕይወት እስትንፋስ፣
በአፍንጫዬም ውስጥ የእግዚአብሔር
መንፈስ እስካለ ድረስ፣
4ከንፈሬ ኀጢአትን አትናገርም፤
አንደበቴም ሽንገላ አይወጣውም::
5እናንተን እንደ ቅኖች መቍጠር፣
የማላደርገው ነገር ነው፤
ጨዋነቴንም እስክሞት ድረስ
አልጥልም::
6ጽድቄን አጥብቄ እይዛለሁ፤ አልለቀውምም፤
በዘመኔም ሁሉ ኅሊናዬ አይወቅሰኝም::

7"ጠላቴ እንደ በደለኛ፣
ባላንጣዬም እንደ ክፉ ይሁን::
8እግዚአብሔር ሲያስወግደው፣
ነፍሱንም ሲወስድበት ዐመፀኛ ምን
ተስፋ አለው?
9በውኑ መከራ በገጠመው ጊዜ፣
እግዚአብሔር ጩኸቱን ይሰማልን?
10ሁሉን በሚችል አምላክ ደስ ይለዋልን?
ዘወትርስ እግዚአብሔርን ይጠራልን?

11"ስለ እግዚአብሔር ክንድ አስተምራችኋለሁ፤
የሁሉን ቻዩንም አምላክ ዕቅድ
አልሸሽግም::
12ሁላችሁ ይህን አይታችኋል፤
ታዲያ፣ ይህ ከንቱ ንግግር ምንድን ነው?

13"እግዚአብሔር ለክፉው የመደበው ዕድል
ፈንታ፣
ግፈኛም ሁሉን ከሚችል አምላክ
የሚቀበለው ቅርስ ይህ ነው:-
14ልጆቹ የቱንም ያህል ቢበዙም ለሰይፍ
ይዳረጋሉ፤
ዘሩም ጠግቦ አያድርም::
15የተረፉለትም በመቅሠፍት አልቀው
ይቀበራሉ፤
መበለቶቻቸውም አያለቅሱላቸውም::
16ብርን እንደ ዐፈር ቢከምር፣
ልብስንም እንደ ሸክላ ጭቃ ቢያከማች፣
17እርሱ ያከማቸውን ጻድቃን ይለብሱታል፤
ብሩንም ንጹሓን ይከፋፈሉታል::
18የሚሠራው ቤት እንደ ሸረሪት ድር፣
እህል ጠባቂም እንደ ቀለሰው መጠለያ
ነው::
19ሀብታም ሆኖ ይተኛል፤ ዘለቄታ ግን የለውም፤
ዐይኑን በገለጠ ጊዜ ሀብቱ ሁሉ በቦታው
የለም::
20ድንጋጤ እንደ ጐርፍ ድንገት
ያጥለቀልቀዋል፤
ዐውሎ ነፋስም በሌሊት ይዞት ይሄዳል::
21የምሥራቅ ነፋስ ይወስደዋል፤ እርሱም
አይገኝም፤
ከስፍራውም ይጠርገዋል::
22ከነፋሱ ብርታት ለማምለጥ ይሮጣል፤
ነገር ግን እየተወረወረ ያለ ርኅራኄ
ይደርስበታል፤
23እጁንም እያጨበጨበ ያሾፍበታል፤
በፉጨትም ከስፍራው ያሽቀነጥረዋል::

# 28

"የብር ማዕድን የሚወጣበት፣
ወርቅም የሚነጠርበት ስፍራ አለ::
2ብረት ከመሬት ውስጥ ይገኛል፤
መዳብም ከማዕድን ድንጋይ ቀልጦ
ይወጣል::
3ሰው፣ እስከ ጨለማ መጨረሻ ይዘልቃል፤
ከድቅድቅ ጨለማ የማዕድን ድንጋይ
ለማግኘት፣
እስከ ውስጠኛው ዋሻ ገብቶ ይፈልጋል::
4የሰው እግር ረግጦት በማያውቅበት ስፍራ፣
ከሰዎች መኖሪያ ርቆ መውረጃ ጕድጓድ
ይቈፍራል፤
ሰው በሌለበት ቦታ ይንጠላጠላል፤
ይወዛወዛል::
5ከላይዋ ምግብን የምታስገኝ ምድር፣
ከታች በእሳት እንደሚሆን

27፥3 ዘፍ2፥7፤ኢዮ 32፥8፤33፥4፤34፥14፤ መዝ144፥4
27፥4 ኢዮ6፥28፤ 12፥16፤16፥17
27፥5 ኢዮ2፥9፤ 10፥7፤32፥2
27፥6 ኢዮ2፥3፤10፥ 7፤23፥10፤29፥14፤ 34፥17፤መዝ119፥ 121፥132፥9፤ኢሳ59፥ 17፤61፥10፥ሐሥ23፥ 1፤ሮሜ2፥15
27፥7 ኢዮ8፥22፤ 31፥35
27፥8 ዘኍ16፥22፤ ኢዮ8፥13፡22፤11፥20፤ ሉቃ12፥20
27፥9 ዘጸ1፥45፤ 1ሳሙ8፥18፤ኢዮ 15፥31
27፥10 ኢዮ22፥26
27፥11 ቍ13፤ኢዮ 36፥23
27፥13 ኢዮ16፥19፤ 20፥29
27፥14 ኢዮ4፥11፤ 5፥4፤15፥22፤ሰቆ2፥22
27፥15 መዝ78፥64
27፥16 1ነገ10፥27፤ ዘካ9፥3
27፥17 ዘፀ3፥22፤ ኢዮ3፥15፤7፥8፤መዝ 39፥6፤49፥10፤ምሳ13 ፥22፤28፥8፤መክ2፥26
27፥18 ኢዮ8፥14፡ 22፤ኢሳ1፥8፤24፥20
27፥19 ኢዮ3፥13፤ 7፥8፤14፥20
27፥20 ኢዮ6፥4፤ 15፥21፤20፥8
27፥21 ኢዮ7፥10፤ 30፥22፤38፥24፤ኤር 13፥24፤22፥22
27፥22 2ነገ7፥15፤ ኢዮ11፥20፤ኤር 13፥14፤ሕዝ5፥11፤ 24፥14
27፥23 ዘኍ24፥10፤ ኢዮ7፥10፤ናሆ3፥19
28፥1 መዝ12፥6፤ 66፥10፤ኤር9፥7፤ዳን11፥35፤ሚል3፥3 28፥2 ዘዳ8፥9 28፥3 ኢዮ 26፥10፤38፥19፤መክ1፥13፤7፥25፤8፥17 28፥4 ቍ10፤2ሳሙ5፥8

27፥5 *እናንተን፤* ኢዮብ በንግግሩ መደምደምያ ላይ ሦስቱን ወዳጆቹን በአንድነት ይናገራቸዋል::

27፥6 *ጽድቄን... እይዛለሁ፤* እግዚአብሔርም ለኢዮብ እንዲሁ መስክሮለታል (2፥3 ይመ)::

27፥7 *ጠላቴ እንደ በደለኛ... ይሁን፤* ኢዮብ፣ በደለኛ ነው ብለው በሐሰት የከሰሱትን ጓደኞቹን፣ ራሳቸው በደለኛ ተብለው እንዲጠሩ ጥሪውን ያቀርባል (ከመዝ 109፥6-15፤ 137፥8-9 ጋር ያነጻጽሩ)::

27፥11 *አስተምራችኋለሁ፤* ኢዮብ፣ ሦስቱም ወዳጆቹ በኀብረት ስለ ተነሡበት በእነዚህ ክፉዎች ሰዎች ላይ የእግዚአብሔር ቍጣ ይመጣባቸው ዘንድ ተገቢ ነበር (ቍ 13-23):: ሦስቱም ወዳጆች ኢዮብን በሐሰት ከክፉዎች ጋር መድበውታል::

*27፥13-23፤* ክፉዎች የሥራቸውን እንዲያገኙ ኢዮብ ለቀረበው ጥሪ (ቍ 7)፣ ውጤቱ ምን እንደ ሆነ ተውኔታዊ በሆነ መልክ የሚያሳይ ግጥም ነው::

*27፥13፤* ሶፋር በ20፥29 ላይ የተናገረውን ቃል፣ ኢዮብ በዚህ ይደግመዋል (በዚያ የሚገኘውን ማብ ይመ)::

27፥18 *ድር... መጠለያ፤* ይህ ጊዜያዊ መሆኑን ያመለክታል (የ4፥19 ማብ፤ የኢሳ 1፥8 ማብ፤ እንዲሁም 24፥4 ይመ)::

27፥21 *የምሥራቅ ነፋስ፤* የ15፥2 ማብ ይመ::

*28፥1-28፤* የሰው ዘር ለምን እንደሚሠቃይ ለመግለጽ የኢዮብ ወዳጆች ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን ጥበብ የተጠቀሙበት ዘዴ አጥጋቢ አልነበረም፤ እንዲያውም ባሕላዊ ያልሆነው አመለካከቱ ከእነርሱ የተሻለ ነበር:: ምስጢርን ግልጽ ለማድረግ የተደረገው የሁለቱም ጥረት ውጤት አላገኘም፤ ውይይቱም አጥጋቢ ባልሆነ ሁኔታ ተደምድሞአል:: ኢዮብ ወይም ስሙ ያልታወቀው የዚህ መጽሐፍ ጸሓፊ ውበትን በተላበሰ ጥበባዊ ቅኔ፣ ይህን ጥያቄ ጣልቃ በማስገባት መልሶታል፤ ይኸውም "ጥበብ ከወዴት ትገኛለች?" (ቍ 12፤ እንዲሁም ቍ 20 ይመ) የሚለው ቅኔ ሦስት ክፍሎች ያሉት ሲሆን፣ (1) የከበሩ ድንጋዮችና ብረታ ብረት የሚገኙት ከጥልቍ የማዕድን ጕድጓድ ነው (ቍ 1-11)፤ (2) ጥበብ ከማዕድን ጕድጓድ አትገኝም፤ በከበረ ድንጋይም ሆነ በብር አትገዛም (ቍ 12-19)፤ (3) ጥበብ የምትገኘው ከእግዚአብሔር ዘንድና እግዚአብሔርን ከመፍራት ነው (ቍ 20-28):: ስለዚህ ይህ ምዕራፍ የእግዚአብሔር ሐሳብ ምን መሆን እንዳለበት ለማወቅ ይገፋፋል (38፥1-42፥6):: ኢዮብና ወዳጆቹ መርምረው ለመድረስ ላቃታቸው ምስጢር ብቸኛው መልስ እግዚአብሔር ነው::

*28፥1-11፤* የጥንቱን የማዕድን ቍፋሮ ዘዴ የሚገልጽ ውብ ግጥም ነው::

28፥2 *ብረት፤* የ19፥24 ማብ ይመ::

28፥3 *እስከ ጨለማ መጨረሻ ይዘልቃል፤* እንደ ችቦና እንደ ፋኖስ ያሉትን ሰው ሠራሽ የብርሃን ምንጮችን በመጠቀም ነው::

28፥4 *ይንጠላጠላል፤ ይወዛወዛል፤* ዛሬም ሆነ ጥንት የማዕድን ቍፋሮ አስቸጋሪና አደገኛ ሥራ ነው፤ ሆኖም ግን ሰዎች በምድር ውስጥ ያለውን ሀብት ቈፍረው ለማውጣት ጥረት ያደርጋሉ::

ትለዋወጣለች::
[6]ሰንፔር[ሀ] ከዐለቷ ይወጣል፤
ከዐፈሯም የወርቅ አንኳር ይገኛል::
[7]ያን መንገድ ጭልፊት አያውቀውም፤
የአሞራም ዐይን አላየውም፣
[8]ኩሩ አራዊት አልረገጡትም፤
አንበሳም በዚያ አላለፈም::
[9]ሰው እጁን በቡላድ ድንጋይ ላይ ያነሣል፤
ተራሮችንም ከሥር ይገለብጣል::
[10]በድንጋይ ውስጥ መተላለፊያ ያበጃል፤
ዐይኖቹም የከበሩ ነገሮችን ሁሉ ያያሉ::
[11]የወንዞችን ምንጭ ይበረብራል፤[ለ]
የተሰወረውንም ነገር ወደ ብርሃን
ያወጣል::

[12]"ነገር ግን ጥበብ ከወዴት ትገኛለች?
ማስተዋልስ መኖሪያዋ የት ነው?
[13]ሰው ዋጋዋን አያውቅም፤
በሕያዋንም ምድር አትገኝም::
[14]ውቅያኖስ፣ 'በእኔ ውስጥ የለችም' ይላል፤
ባሕርም፣ 'በእኔ ዘንድ አይደለችም'
ይላል::
[15]ንጹሕ ወርቅ ሊገዛት አይችልም፤
ዋጋዋም በብር አይመዘንም::
[16]በኦፊር ወርቅ፣
በከበረም መረግድና በሰንፔር
አትገመትም::
[17]ወርቅም ብርሌም አይወዳደሯትም፤
በወርቅ ጌጥም አትለወጥም::
[18]ዛጒልና አልማዝ ከቍጥር አይገቡም፤
የጥበብ ዋጋ ከቀይ ዕንቍም ይበልጣል::
[19]የኢትዮጵያ ቶጳዝዮን ሊስተካከላት
አይችልም፤
ዋጋዋም በንጹሕ ወርቅ አይተመንም::

[20]"ታዲያ፣ ጥበብ ከወዴት ትመጣለች?
ማስተዋልስ የት ትገኛለች?
[21]ከሕያዋን ፍጥረታት ዐይን ሁሉ
ተሰውራለች፤
ከሰማይ ወፎችም ተሸሽጋለች::
[22]ጥፋትና[ሐ] ሞት፣
'ወሬዋን ብቻ ሰማን' ይላሉ::
[23]ወደ እርሷ የሚወስደውን መንገድ
የሚረዳ፣
መኖሪያዋንም የሚያውቅ እግዚአብሔር
ብቻ ነው፤
[24]እርሱ የምድርን ዳርቻ ይመለከታልና፤
ከሰማይ በታች ያለውንም ሁሉ ያያል::
[25]ለነፋስ ኀይልን በሰጠ ጊዜ፣
የውሆችን መጠን በለካ ጊዜ፣
[26]ለዝናብ ሥርዐትን፣
ለነጎድጓድም መንገድን ባበጀ ጊዜ፣
[27]በዚያን ጊዜ ጥበብን ተመለከታት፤
ገመገማትም፤
አጸናት፤ መረመራትም::
[28]ከዚያም ሰውን፣
'እግዚአብሔርን መፍራት ጥበብ ነው፤
ከክፋትም መራቅ ማስተዋል ነው' አለው::"

# 29

ኢዮብም እንዲህ ሲል ንግግሩን ቀጠለ፤
[2]"በእግዚአብሔር የተጠበቅሁበትን ዘመን፣
ያለፈውንም ወራት ምንኛ ተመኘሁ!
[3]ያን ጊዜ መብራቱ በራሴ ላይ ይበራ ነበር፤
በብርሃኑም በጨለማ ውስጥ ዐልፌ እሄድ
ነበር፤
[4]እኔም ብርቱ ነበርሁ፤
የእግዚአብሔርም ወዳጅነት ቤቴን ይባርክ
ነበር፤

28፥5 ዘፍ1፥29፤መዝ104፥14፤145፥15 28፥6 ቍ16፤ኢዮ22፥24፤መሕ5፥14፤ኢሳ54፥11 28፥7 ቍ21 28፥8 ኢዮ41፥34፤ኢሳ35፥9 28፥9 ዘዳ8፥15፤ዮና2፥6 28፥10 ቍ4፤ምሳ2፥4 28፥11 ዘፍ7፥11፤ኢሳ48፥6፤ኤር33፥3 28፥12 ቍ20፡23፡28፤ምሳ1፥20፤3፥13-20፤8፥1፤9፥1-3፤መክ7፥24 28፥13 ዘዳ29፥29፤መዝ27፥13፤52፥5፤116፥9፤142፥5፤ምሳ3፥15፤ኢሳ38፥11፤ኤር11፥19፤ሕዝ26፥20፤32፥24፤ማቴ13፥44-46 28፥14 ዘዳ30፥13፤መዝ42፥7፤ሮሜ10፥7 28፥15 ቍ17፤ምሳ3፥13-14፤8፥10-11፤16፥16፤ሐሥ8፥20 28፥16 ቍ6፤ዘፍ10፥29፤ዘፀ24፥10 28፥17 ቍ15፤መዝ119፥72፤ምሳ8፥10 28፥18 ምሳ3፥15፤8፥11፤ሕዝ27፥16፤ራእ21፥11 28፥19 ዘፀ28፥17፤ምሳ3፥14-15፤8፥10-11፡19፤ኢሳ11፥11 28፥20 ኢዮ9፥4 28፥21 ቍ7 28፥22 ኢዮ20፥26፤ምሳ8፥32-36፤ራእ9፥11 28፥23 ኢዮ9፥4፤22፥22፤ምሳ8፥22-31፤መክ3፥11፤8፥17 28፥24 ኢሱ3፥11፤ኢዮ10፥4፤36፥32፤37፥3፤38፥18፡24፡35፤መዝ33፥13-14፤66፥7፤ኢሳ11፥12፤ዕብ4፥13 28፥25 ኢዮ12፥15፤38፥8-11 28፥26 ኢዮ36፥28፡33፤37፥3፡6፡8፡11፤38፥27፤መዝ65፥12፤104፥14፤147፥8፤ኢሳ35፥7፤ኤር51፥16 28፥27 ምሳ3፥19፤8፥22-31 28፥28 ዘፀ20፥20፤ዘዳ4፥6፤ኢዮ37፥24፤መዝ111፥5፤97፥10፤ምሳ3፥7፤ 8፥13 29፥1 ኢዮ27፥1 29፥2 ዘፍ31፥30፤ኤር1፥12፤31፥28፤44፥27 29፥3 ኢዮ11፥17፤12፥25 29፥4 ኢዮ15፥8፤መዝ25፥14፤ምሳ3፥32

[ሀ]6 በዚህና በቍ 16 ላይ፣ *ላፒስ ላዙሊ*
[ለ]11 የሰብዓ ሊቃናት ትርጒምና ቩልጌት ከዚህ ጋር ይስማማል፤ ዕብራይስጡ ግን *ይገድባል* ይላል
[ሐ]22 ዕብራይስጡ፣ *ዐባዶን* ይላል

28፥6 *ሰንፔር፤* ቍ 16፤ እንዲሁም የማሕ 5፥14፤ የኢሳ 54፥11 ማብ ይመ::

28፥9 *ተራሮችንም ከሥር፤* ጥልቀትን ለመግለጽ የገባ ቅኔያዊ አገላለጽ ነው (ከዮና 2፥6 ጋር ያነጻጽሩ)::

28፥10 *በድንጋይ ውስጥ መተላለፊያ፤* በስምንተኛው ምእተ ዓ.ቅ.ክ. ኢየሩሳሌም፣ በሰሊሆም መጠመቂያ የተገኘው ጽሑፍ የጥንቱን የመሬት ውስጥ ለውስጥ የመንገድ ሥራ ከፍተኛ ደረጃ መድረሱን የሚያመለክት ነው::

*28፥12፤* በቍ 20 ላይ የተነሡት እነዚህ ጥያቄዎች በቍ 28 ላይ መልስ አግኝተዋል::

28፥16 *በኦፊር ወርቅ፤* 22፥24 ማብ ይመ::

28፥18 *የጥበብ ዋጋ ከቀይ ዕንቍም ይበልጣል፤* (ምሳ 31፥10)፣ እግዚአብሔርን በመፍራቷ (ምሳ 31፥10) ጥበበኛ የሆነች (ቍ 28) ጠባየ መልካም ሚስት ዋጋ ነው ::

28፥19 *ኢትዮጵያ፤* ከግብፅ በስተ ደቡብ የሚገኝ የዐባይ ላይኛው ክፍል ነው::

28፥21 *ተሰውራለች... ወፎችም፤* እንደ ውድ ብረቶችና የከበሩ ድንጋዮች ማለት ነው (ቍ 7 ይመ)::

28፥22 *ጥፋትና ሞት፤* የ26፥6 ማብ ይመ::

*28፥25-27፤* ፍጥረት እውን በሆነበት ጊዜም እንኳ፣ ጥበብ በእግዚአብሔር ዘንድ ነበረች (ምሳ 8፥22-31 ይመ)::

28፥28 *እግዚአብሔርን መፍራት... ከክፋትም መራቅ፤* የኢዮብ ባሕርይ የተገለጸበትን ክፍል 1፥1፡8፤ 2፥3 ይመ:: *ጥበብ ነው፤* "እግዚአብሔርን መፍራት የጥበብ መጀመሪያ ነው" (መዝ 111፥10፤ ምሳ 9፥10፤ እንዲሁም ምሳ 1፥7 ይመ)::

*29፥1-30፥40፤* አንድ ጠበቃ የመጨረሻ ሐሳቡን አጠቃሎ እንደሚያቀርብ ሁሉ፣ ኢዮብም በሦስት ምድብ የተከፈለ ማጠቃለያ ያቀርባል፤ የመጀመሪያው ክፍል (ም 29)፣ "እንዴት ያማረ ነበር!" በሚል የቀደመውን የሐሤት ዘመኑን፣ ማለትም ሀብቱንና የነበረ ክብሩን ዘወር ብሎ ያስታውሳል፤ ሁለተኛው ክፍል (ም 30) ንብረቱና ሀብቱ በተለይም ክብሩ ሁሉ እንዳልነበረ ስለ ሆነበት በሰቆቃ ስሜቱን ይገልጻል፤ እንዲሁም በክፍል ሦስት (ም 31) ከበደል ነጻ እንደ ሆነ ይገልጻል::

*29፥1-25፤* ይህ ምዕራፍ ለሴማዊ ሥነ ጽሑፍ ውበት ዐይነተኛ ምሳሌ ነው፤ በዚህም ውስጥ ቡራኬን (ቍ 2-6)፣ ሙገሳን (ቍ 7-10)፣ ርኅራኄን (11-17)፣ ዳግም ቡራኬ (18-20) እና ሙገሳ (21-25) እያለ ቃላቱን በጽሑፍ ውስጥ መላልሶ ሲደጋግም እናያለን::

*29፥2-6፤* በስሜት የሆነ ንግግር ነው፤ በመጀመሪያዎቹ ቀናት እግዚአብሔር የኢዮብ የቅርብ ወዳጁ ነበር::

29፥3 *በብርሃኑም... እሄድ ነበር፤* የ22፥28 ማብ ይመ::

29፥4 *የእግዚአብሔርም ወዳጅነት ቤቴን ይባርክ ነበር፤* በቀጥታ፣ "የእግዚአብሔር ጉባኤ በድንኳኔ ዙሪያ ሳለ" ወይም "በድንኳኔ ውስጥ እግዚአብሔር የቅርብ ወዳጅ ሆኖልኝ ሳለ" ማለት ነው:: ይህ ዐረፍተ ነገር በዘፍ 18 ላይ የተጠቀሰውን ታሪክ ያሳስባል፤ ይኸውም እግዚአብሔርና ሁለት የእርሱ መላእክት በአ

[5]ሁሉን የሚችል አምላክ ከእኔ ጋር ነበረ፤
ልጆቼም በዙሪያዬ ነበሩ፤
[6]መንገዴ በቅቤ የራሰ ነበር፤
ዐለቱም የወይራ ዘይት ያመነጭልኝ
ነበር።
[7]"ወደ ከተማዪቱ በር ብቅ ባልሁ ጊዜ፣
በአደባባይዋም በወንበር በተቀመጥሁ ጊዜ፣
[8]ጐበዛዝት አይተውኝ ገለል ይሉ፣
ሽማግሌዎችም ተነሥተው ይቆሙ ነበር።
[9]የሰፈሩ ታላላቅ ሰዎች ከመናገር ይቈጠቡ፣
እጃቸውንም በአፋቸው ላይ ይጭኑ
ነበር፤
[10]የመኳንንት ድምፅ ጸጥ ይል፣
ምላሳቸውም ከላንቃቸው ጋር ይጣበቅ
ነበር፤
[11]የሰሙኝ ሁሉ ያሞጋግሱኝ፣
ያዩኝም ያመሰግኑኝ ነበር፤
[12]ለርዳታ የሚጮኸውን ችግረኛ፣
ድኻ ዐደጉንም ታድጌአለሁና።
[13]በሞት አፋፍ ላይ የነበረ መርቆኛል፤
የመበለቲቱንም ልብ አሳርፌአለሁ።
[14]ጽድቅን እንደ ልብስ ለበስሁ፤
ፍትሕም መጐናጸፊያዬና ጥምጥሜ
ነበር።
[15]ለዕውራን ዐይን፣
ለአንካሶችም እግር ነበርሁ።
[16]ለችግረኛው አባት፣
ለባይተዋሩ ተሟጋች ነበርሁ።
[17]የኀጢአተኛውን ክራንቻ ሰበርሁ፤
የነጠቀውንም ከጥርሶቹ አስጣልሁ።
[18]"እኔም በልቤ እንዲህ አልሁ፤ 'ዘመኔ
እንደ አሸዋ በዝቶ፣
በቤቴ ተደላድዬ እሞታለሁ፤
[19]ሥሬ ወደ ውሃ ይዘረጋል፤
ጠልም በቅርንጫፌ ላይ ያድራል፤
[20]ክብሬ በውስጤ አዲስ እንደ ሆነ፣
ቀስትም በእጄ እንደ በረታ ይኖራል።'
[21]"ሰዎች ምክሬን በጸጥታ በመጠባበቅ፣
በጕጕት አዳመጡኝ።
[22]እኔ ከተናገርሁ በኋላ፣ የሚናገር ሰው
አልነበረም፤
ቃሌም እየተንጠባጠበ በጆሯቸው ይገባ
ነበር።
[23]ዝናብ እንደሚጠብቅ ሰው ጠበቁኝ፤
ቃሌንም እንደ በልግ ዝናብ ጠጡ፤
[24]በሣቅሁላቸው ጊዜ እውነት
አልመሰላቸውም፤
የፊቴም ብርሃን ብርቅ ሆነባቸው[a] ነበር።
[25]መንገድ መርጬላቸው አለቃቸው ሆኜ
ተቀመጥሁ፤
በሰራዊትም መካከል እንዳለ ንጉሥ
ኖርሁ፤
ሐዘንተኞችንም እንደሚያጽናና ነበርሁ።

# 30

"አሁን ግን በዕድሜ ከእኔ የሚያንሱ፣
ከመንጋዬ ጠባቂ ውሾች ጋር
እንዳይቀመጡ፣
አባቶቻቸውን የናቅኋቸው፣
እነዚህ ይሣለቁብኛል።
[2]ጕልበት የከዳቸው፤
የክንዳቸው ብርታት ምን ፋይዳ
ይሞላልኝ ነበር?
[3]ከችጋርና ከራብ የተነሣ ጠወለጉ፤
ሰው በማይኖርበት በረሓ፣
በደረቅም ምድር በሌሊት ተንከራተቱ።[b]
[4]ከቍጥቋጦ ምድር ጨው ጨው የሚል
አትክልት ለቀሙ፤
ምግባቸውም የክትክታ ሥር ነበር።
[5]ከኅብረተ ሰቡ ተለይተው ተባረሩ፤
ሰዎች እንደ ሌባ ይጮኹባቸዋል።
[6]በዐለት መካከል በምድር ጕድጓድ፣
በደረቅ ሸለቆ ዋሻ ውስጥ ለመኖር
ተገደዱ።
[7]በጫካ ውስጥ ያናፋሉ፤
በእሾሃማ ቍጥቋጦ መካከልም
ይታፈጋሉ።
[8]ስማቸው የማይታወቅ አልባሌ ናቸው፤
ከምድሪቱም ተባረዋል።

29፥5 ሩት4፥1፤ መዝ127፥3-5፤128፥3
29፥6 ዘፍ49፥20፤ ዘዳ32፥13፤ኢዮ20፥17፤መዝ81፥16
29፥7 ቍ21፤ኢዮ5፥4፤31፥21፤ኤር20፥2፤38፥7
29፥8 ዘሌ19፥32፤1ጢሞ5፥1
29፥9 ቍ21፤መሳ18፥19፤ኢዮ31፥21፤40፥4፤ምሳ30፥32
29፥10 ቍ22፤መዝ137፥6
29፥11 ኢዮ4፥4፤ዕብ11፥4
29፥12 ዘዳ24፥17፤ ኢዮ24፥4፤31፥17፡21፤ መዝ72፥12፤ምሳ21፥13
29፥13 ዘዳ10፥18፤ ኢዮ22፥9፤31፥20
29፥14 2ሳሙ8፥15፤ኢዮ19፥9፤27፥6፤ ኤፌ4፥24፤6፥14
29፥15 ዘኍ10፥31፤ ኢዮ4፥4
29፥16 ዘፀ18፥26፤ ኢዮ4፥4፤24፥4፤ምሳ22፥22-23
29፥17 ኢዮ4፥10፡ 11፤24፥9፤መዝ3፥7
29፥18 መዝ1፥1-3፤ 15፥5፤16፥8፤30፥6፤62፥2፤139፥18፤ምሳ3፥1-2
29፥19 ዘፍ27፥28፤ ዘኍ24፥6፤ኢዮ14፥9፤15፥30፤መዝ133፥3
29፥20 ዘፍ49፥24፤ ኢዮ30፥11፤መዝ18፥34፤92፥14፤ኢሳ38፥12
29፥21 ቍ7፡9
29፥22 ቍ10፤ ዘዳ32፥2
29፥23 ኢዮ4፥3
29፥24 ዘኍ6፥25፤ ምሳ16፥14፡15
29፥25 ኢዮ1፥3፤ 4፥4፤21፥28
30፥1 ኢዮ6፥14፤ 11፥3፤መዝ119፥21፤ ኢሳ56፥10
30፥3 ኢዮ24፥5፤ ኢሳ8፥21፤ኤር17፥6
30፥4 1ነገ19፥4፤ ኢዮ39፥6 30፥6 ኢሳ2፥19፤ሆሴ10፥8 30፥7 ኢዮ6፥5፤39፥5-6
30፥8 መሳ9፥4፤ኢዮ18፥18

[a]24 በዕብራይስጡ የዚህ ሐረግ ትርጕም በትክክል አይታወቅም
[b]3 ወይም ተመቃጹ

ብርሃም ድንኳን ውስጥ ምግብ ቀርበላቸው መብላታቸውን፣ እግዚአብሔርም እስጥሃለሁ ስላለው ወንድ ልጅ እንዲሁም ስለ ሰዶምና ገሞራ ያለውን ዕቅድ ለወዳጁ መግለጹን የሚያመለክት ነው።

29፥5 *ልጆቼም በዙሪያዬ ነበሩ፤* 1፥2 ይመ።

29፥6 *በቅቤ... የወይራ ዘይት፤* የባለጸግነትና የምቾት ምልክት ነው (20፥17፤ ሕዝ 16፥19 ይመ)።

29፥7 ... *ከተማዪቱ በር፤* ታላላቅ የንግድ ሥራዎችና የፍርድ ውሳኔዎች የሚከናወኑባት ቦታ ነበረች (የሩት 4፥1 ማብ ይመ)። *በተቀመጥሁ ጊዜ፤* የከተማ ሽማግሌዎች ወይም የአመራሩ አካል አባላት ማለት ነው (የዘፍ 19፥1 ማብ ይመ)።

29፥12-13 *ደኻ ዐደጉንም ታድጌአለሁና... የመበለቲቱንም ልብ አሳርፌአለሁ፤* ኤልፋዝ በ22፥9 ላይ ለቀረበበት ክስ ኢዮብ በደፈናው መልስ በመስጠት ለድኻ አደጉና ለችግረኛው ያለውን ሐዘኔታ ይገልጻል (24፥9፤ 31፥16-18፡21 ይመ)።

29፥14 *ጽድቅን... ለበስሁ፤ ፍትሕም መጐናጸፊያዬና፤* ከዚሁ ጋር ተመሳሳይ የሆነውን ስዕላዊ አገላለጽ በኢሳ 59፥17፤ 61፥10፤ ኤፌ 6፥14፡17 ይመ።

29፥18 *በልቤ እንዲህ አልሁ፤* ኢዮብ ሕይወቱ ምን ሊሆን እንደሚችል በጥልቀት ያሰባል።

*29፥21-25፤* የኢዮብ ምክር ተቀባይነት አገኘ (ቍ 21-23)፤ አስተያየቱ ጠቃሚ ሆነ (ቍ 24)፤ አመራሩንም በምስጋና ተቀበሉት (ቍ 25)።

*30፥1-31፤ ም* 29 ትክክለኛ ስለ ሆነ በረከትና ሞገስ ያወራል፤ ይህ ምዕራፍ ግን ኢዮብ ያለፈበትን ሥቃይና ውርደት ያሳያል። ኢዮብ በከባድ ድንጋጤ ውስጥ እንዲያልፍ እግዚአብሔር ፈቅዶአል፤ በመጨረሻም ኢዮብ ያሰማው ሰቆቃ (ቍ 15)፣ የደረሰበት ሥቃይ ምን ያህል አስመርሮት እንደ ነበር (ቍ 31) ያመለክታል።

30፥1፡9 *አሁን ግን... ይሣለቁብኛል፤* ቀደም ሲል ወጣቱም ሆነ ሽማግሌው ተገቢውን ክብር ይሰጠው ነበር (29፥8-11፡ 21-25 ይመ)።

30፥4 *ጨው ጨው... አትክልት፤* ኢዮብና ወዳጆቹ በኖሩበት፣ ከሲና በስተ ምሥራቅ በሚገኘው አካባቢ የሚበቅል ተክል ሳይሆን አይቀርም፤ ከ39፥6 ጋር ያነጻጽሩ። *የክትክታ ሥር፤* በመካከለኛው ምሥራቅና በዐረብ በረሓዎች የሚበቅል ትልቅ ዛፍ ነው (1ነገ 19፥4፤ መዝ 120፥4 ይመ)።

[9]"አሁን ግን ልጆቻቸው በዘፈን
ይሣለቁብኛል፤
በእነርሱም ዘንድ መተረቻ ሆኛለሁ።
[10]ይጸየፉኛል ወደ እኔም አይቀርቡም፤
ያለ ምንም ይሉኝታ በፊቴ ይተፋሉ።
[11]እግዚአብሔር የቀስቴን አውታር ስላላላውና
በመከራም ስለ መታኝ፣
በፊቴ መቈጠብን ትተዋል።
[12]በቀኜ በኩል ባለጌዎች[a] ሆ! ብለው
ተነሡብኝ፤
ለእግሬም ወጥመድ ዘረጉ፤
የዐፈር ድልድልም አዘጋጁብኝ።
[13]መንገድ ዘጉብኝ፤
የሚገታቸው[b] ሳይኖር፣
ሊያጠፉኝ ተነሡ።
[14]በሰፊ ንቃቃት ውስጥ እንደሚመጣ ሰው
መጡብኝ፤
በፍርስራሽም መካከል እየተንከባለሉ
ደረሱብኝ።
[15]በድንጋጤ ተውጫለሁ፤
ክብሬ በነፋስ እንደሚወሰድ ተወስዶአል፤
በሰላም መኖሬም እንደ ደመና እልም
ብሎ ጠፍቶአል።
[16]"አሁን ነፍሴ በውስጤ አለቀች፤
የመከራ ዘመንም ይዞኛል።
[17]ደዌ በሌሊት ዐጥንቴን ይበሳል፤
የሚቈረጥመኝም ፋታ አይሰጠኝም።
[18]እግዚአብሔር በታላቅ ኀይሉ ልብሴን[c]
ጨምድዶአል፤
በልብሴም ክሳድ አንቆ ይዞኛል።
[19]እርሱ ጭቃ ውስጥ ጥሎኛል፤
እኔም ከዐፈርና ከዐመድ አልተሻልሁም።
[20]"እግዚአብሔር ሆይ፤ ወደ አንተ ጮኽሁ፤
ነገር ግን አልመለስህልኝም፤
በፊትህም ቆምሁ፤ አንተ ግን ዝም
አልኸኝ።

[21]ተመልሰህ ጨካኝ ሆንህብኝ፤
በክንድህም ብርታት አስጨነቅኸኝ።
[22]ወደ ላይ ነጥቀህ በነፋስ ፊት አበረርኸኝ፤
በዐውሎ ነፋስም ወዲያ ወዲህ
ወዘወዝኸኝ።
[23]ለሕያዋን ሁሉ ወደ ተመደበው ስፍራ፣
ወደ ሞት እንደምታወርደኝ ዐውቃለሁ።
[24]"የተጐዳ ሰው ተጨንቆ ድረሱልኝ ብሎ
ሲጮኽ፣
በእርግጥ ክንዱን የሚያነሣበት ማንም
የለም።
[25]በመከራ ውስጥ ላሉት አላለቀስሁምን?
ለድኾችስ ነፍሴ አላዘነችምን?
[26]ነገር ግን መልካም ስጠብቅ፣ ክፉ ነገር
ደረሰብኝ፤
ብርሃንንም ስጠባበቅ፣ ጨለማ መጣብኝ።
[27]በውስጤ ያለው ነውጥ አላቋረጠም፤
የመከራ ዘመንም መጣብኝ።
[28]በፀሓይ አይደለም እንጂ፣ ጠቋቍሬ
እዞራለሁ፤
በጉባኤ መካከል ቆሜ ለርዳታ እጮኻለሁ።
[29]የቀበሮች ወንድም፣
የጕጕቶችም ባልንጀራ ሆኛለሁ።
[30]ቈዳዬ ጠቍሮ ተቀረፈ፤
ዐጥንቴም በትኩሳት ነደደ።
[31]በገናዬ ለሐዘን፣
እምቢልታዬም ለልቅሶ ተቃኝቶአል።

# 31

"ወደ ኰረዳዪቱ ላለመመልከት፣
ከዐይኔ ጋር ቃል ኪዳን ገብቻለሁ።

30፥9 ኢዮ12፥4፤16፥10፥17፥6፤መዝ69፥11፤ሰቆ3፥14፡63
30፥10 ዘዳ25፥9፤ኢዮ19፥19፤ማቴ26፥67
30፥11 ዘፍ12፥17፤ሩት1፥21፤ኢዮ29፥20፤41፥13፤መዝ32፥9
30፥12 ኢዮ16፥10፥18፥9፤መዝ109፥6፤140፥4-5፤ዘካ3፥1
30፥13 ኢዮ10፥3፤ኢሳ3፥12
30፥14 2ነገ25፥4
30፥15 ዘፀ3፥6፤ኢዮ3፥25፤6፥4፤10፥8፤31፥2-3፡23፤መዝ55፥4-5
30፥16 ቍ27፤ኢዮ3፥24፤9፥17
30፥17 ዘዳ28፥35፤ኢዮ16፥16
30፥18 ኢዮ9፥4
30፥19 ዘፍ3፥19፤ኢዮ2፥8፤መዝ40፥2፤69፥2፡14፤130፥1፤ኤር38፥6፡22
30፥20 1ነገ8፥52፤ኢዮ19፥7፤መዝ34፥17፤ምሳ2፥3፤ሰቆ3፥8፤ሚክ4፥9
30፥21 ኢዮ4፥5፤6፥4፤10፥3፤ኢሳ9፥12፤14፥26፤31፥3፤ኤር6፥23፤30፥14፤50፥42፤ሕዝ6፥14
30፥22 ኢዮ9፥17፤27፥21፤ይሁ1፥12
30፥23 2ሳሙ14፥14፤ኢዮ3፥13፡19፤10፥3
30፥24 ኢዮ19፥7፤መዝ145፥14፤ኢሳ42፥3፤57፥15
30፥25 ኢዮ24፥4፤መዝ35፥13-14፤ሉቃ19፥41፤ሮሜ12፥15፤ፊል3፥18
30፥26 ኢዮ3፥6፡17፤19፥8፤መዝ82፥5፤ኤር4፥23
30፥27 ቍ16፤መዝ38፥8፤ሰቆ2፥11 30፥28 ኢዮ17፥14፤19፥7፤24፥12፤ሰቆ4፥8 30፥29 መዝ44፥19፤102፡6፤ኢሳ34፥13፤ኤር9፥11፤ሚክ1፥8 30፥30 ዘዳ28፥35፤ኢዮ16፥16፤17፥14፤መዝ102፥3፤ሰቆ1፥13፤3፥4፤4፥8፤5፥10 30፥31 ዘፍ4፥21፥8፥8፤መዝ137፥2፤ኢሳ16፥11፤24፥8፤ሕዝ26፥13

[a]12 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም በትክክል አይታወቅም
[b]13 ወይም *'ማንም ሊረዳው አይችልም' አሉ*
[c]18 የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ከዚህ ጋር ይስማማል፤ ዕብራይስጡ ግን፣ *እንደ ልብስ ሆኖብኛል* ይላል።

30፥9 *መተረቻ፤* የ17፥6 ማብ ይመ።

30፥11 *እግዚአብሔር የቀስቴን አውታር ስላላላውና፤* ኢዮብ ቀስቱ አዲስና ጠንካራ ለመሆኑ እርግጠኛ ከሆነበት ከ29፥20 ጋር የሚጻረር ነው።

30፥12 *የዐፈር ድልድልም፤* 19፥12 ይመ።

30፥14 *ንቃቃት፤* በከተማ ቅጥር ላይ የሚገኝ ነው።

30፥15 *በነፋስ እንደሚወሰድ፤* ቍ 22 ይመ።

30፥17 *የሚቈረጥመኝም፤* የ2፥7 ማብ ይመ።

30፥18 ... *በልብሴም ክሳድ፤* ጠባብ አንገትጌ ነው።

30፥19 *ከዐፈርና ከዐመድ፤* የውርደትና የዋጋ ቢስነት ምልክት ነው (የዘፍ 18፥27 ማብ ይመ)። ከጊዜ በኋላ ኢዮብ፣ "ትቢያንና ዐመድን" የንስሓ ምልክት አድርጎ ተጠቅሞበታል (42፥6)።

*30፥20-23፤* ኢዮብ አሁን ዐይኖቹን ከሰው ላይ አንሥቶ በእግዚአብሔር ላይ አድርጎአል፤ ምሕረት እንዲያደርግለት ወደ እግዚአብሔር ቢጮኽም እንኳ፣ እግዚአብሔር ግን ዝም ስላለው ጌታን ያማርራል።

*30፥24፤* ከእግዚአብሔርም ሆነ ከሰው ፍትሕ እንዳላገኘ ኢዮብ ይሰማዋል።

*30፥26፤* ከኢሳ 5፥2፡7 ጋር ያነጻጽሩ።

30፥28 *ጠቋቍሬ፤* ቍ 30፤ የ2፥7 ማብ ይመ።

30፥29 *የቀበሮች ወንድም፣ የጕጕቶች ባልንጀራ፤* ነቢዩ ሚክያስ በሚክ 1፥8 ላይ ስለ ራሱ ተመሳሳይ የሆነ ስዕላዊ ገለጻ ይጠቀማል።

30፥30 *በትኩሳት፤* የ2፥7 ማብ ይመ።

*31፥1-40፤* በሦስት ክፍል ከተከፈለው የኢዮብ የማጠቃለያ ንግግር ውስጥ ይህ ከፍተኛውን ደረጃ የያዘ ነው (የ29፥1-31፡40 ማብ ይመ)፤ ኢዮብ የተዘረዘሩትን ኀጢአቶች አልፈጸምሁም በማለቱ ክፍሉ አሉታዊ ስሜት ያለው ቢመስልም እንኳ ሉዓላዊ አምላክ እንደ መሆኑ መጠን ለእርሱ ያለውን ታማኝነት በማሳየቱ ረገድ ሲታይ አወንታዊ ዐላማ አለው። ኢዮብ ጠንከር ባለ በፍርድ ቤት ቋንቋ፣ "እውነት ይህን አድርጌው ከሆነ ይህ ይድረስብኝ" በማለት፣ የመከላከያ ሐሳቡን አጠናቆ ያቀርባል። ከዚህ በተረፈ የሚባል ነገር የለም (ቍ 40)፤ እዚህም ላይ ላቀረበው ማረጋገጫ የማጽደቂያ መልክቱን በፊርማ መልክ ያስቀምጣል (ቍ 35)። ጉስቋላ ኀጢአተኛ ስለ መሆኑ ወይም ስላለመሆኑ የማረጋገጡ ኀላፊነት ያለው በእግዚአብሔር እጅ ነው። ኢዮብ ንጹሕ ሰው መሆኑ ይረጋገጥለት ዘንድ ያቀረበውን አቤቱታ በ27፥2-6 ላይ ከፍተኛ አጽንዖት ሰጥቶታል። ይህንኑ ጽኑ ሐሳብ አጕልቶ የሚያሳየውም በማንኛውም ረገድ የጽድቅ ሕይወት የሚኖር መሆኑን በመግለጽ ነው። ለእያንዳንዱ ማስተባበያ ሐሳብ (ቍ 5-7፡9፡13፡16-21፡24-27፡29-34፡38-39) አጽንዖት የሰጠው፣ ለሚፈጸም በደል ተገቢ የሆነው ቅጣት፣ "ይድረስብኝ" የሚለው መሐላ በማስከተል ነው (ቍ 8፡10-12፡14-15፡22-23፡28፡40)፤ እዚህ ላይ እንደ መርሕ ሆኖ የቀረበው፣ "ሁሉም የእጁን ያገኛል" የሚለው ነው (ዘፀ 21፥23 እና ማብ ይመ)።

*31፥1-12፤* ኢዮብ የልብ ውስጥ ኀጢአት በተለይም በሥጋ ፍትወት (ቍ1-4)፣ በንግድ ማታለል (ቍ5-8)፣ እንዲሁም ለቃል ኪዳን ጋብቻ ታማኝ ሆኖ ባለመገኘት ይጀምራል (ቍ 9-10)።

*31፥1፤ ወደ ኰረዳዪቱ ላለመመልከት፤* በምኞት መመልከቱ ኀጢአት በመሆኑ ነው (ማቴ 5፥28)።

[2]ከላይ ከእግዚአብሔር ዘንድ የሰው ዕድል
ፈንታው፣
ከአርያም ሁሉን ከሚችል አምላክስ
ዘንድ ቅርሱ ምንድነው?
[3]ለኀጢአተኞች ጥፋት፣
ክፉ ለሚያደርጉም መቅሠፍት
አይደለምን?
[4]እርሱ መንገዴን አያይምን?
እርምጃዬንስ ሁሉ አይቈጥርምን?

[5]"በሐሰት ሄጄ እንደ ሆነ፣
እግሬም ወደ ሽንገላ ቸኵሎ ከሆነ፣
[6]እግዚአብሔር በእውነተኛ ሚዛን ይመዝነኝ፤
ነውር እንደሌለብኝም ይወቅ::
[7]እርምጃዬ ከመንገድ ወጣ ብሎ፣
ልቤ ዐይኔን ተከትሎ፣
ወይም እጄ ረክሶ ከሆነ፣
[8]የዘራሁትን ሌላ ይብላው፤
ሰብሌም ተነቅሎ ይጥፋ::

[9]"ልቤ ሌላዋን ሴት ከጅሎ፣
በባልንጀራዬ ደጅ አድብቼ ከሆነ፣
[10]ሚስቴ የሌላ ሰው እህል ትፍጭ፤
ሌሎች ሰዎችም ይተኟት፤
[11]ይህ አሳፋሪ፣
ፍርድም የሚገባው ኀጢአት ነውና::
[12]ይህ የሚያቃጥልና የሚያጠፋ[ሀ] እሳት ነው፤
ቡቃያዬንም ሊነቃቅል ነበር::

[13]"ወንዶችና ሴቶች አገልጋዮቼ አቤቱታ
ባቀረቡ ጊዜ፣
ፍርድ አዛብቼ ከሆነ፣
[14]እግዚአብሔር ሲነሣ ምን አደርጋለሁ?
ሲጠይቀኝስ ምን መልስ እሰጣለሁ?
[15]እኔን በማሕፀን ውስጥ የፈጠረኝ እነርሱን
የፈጠረ አይደለምን?
በሆድ ውስጥ የሠራንስ እርሱ ራሱ
አይደለምን?

[16]"ለድኻ የሚያስፈልገውን ከልክዬ ከሆነ፣
ወይም የመበለቲቱን ዐይን አፍዝዤ
ከሆነ፣
[17]እንጀራዬን ከድኻ አደጉ ጋር ሳልካፈል፣
ለብቻዬ በልቼ ከሆነ፣
[18]ይልቁን ድኻ አደጉን ከታናሽነቴ ጀምሮ
እንደ አባት አሳደግሁት፤
መበለቲቱንም ከተወለድሁ ጀምሮ
መንገድ መራኋት፤
[19]በልብስ ዕጦት ሰው ሲጠፋ፣
ወይም ዕርቃኑን ያልሸፈነ ድኻ አይቼ፣
[20]በበጎቼ ጠጕር ስላሞቅሁት፣
ልቡ ባርኮኝ ካልሆነ፣
[21]በአደባባይ ተሰሚነት አለኝ ብዬ፣
በድኻ አደጉ ላይ እጄን አንሥቼ ከሆነ፣
[22]ትከሻዬ ከመጋጠሚያው ይነቀል፤
ክንዴም ከመታጠፊያው ይሰበር፤
[23]የእግዚአብሔርን ቍጣ በመፍራቴ፣
እንዲህ ያሉ ነገሮች መፈጸም
አልቻልሁም::

[24]"ወርቅን ተስፋ አድርጌ፣
ወይም ንጹሑን ወርቅ፣ 'አንተ
መታመኛዬ ነህ' ብዬ ከሆነ፣
[25]እጄ ባገኘችው ሀብት፣
በባለጠግነቴም ብዛት ደስ ብሎኝ ከሆነ፣
[26]የፀሓይን ድምቀት አይቼ፣
ወይም የጨረቃን አካሄድ ግርማ
ተመልክቼ፣
[27]ልቤ በስውር ተታልሎ፣
ስለ ክብራቸው አፌ እጄን ስሞ ከሆነ፣
[28]ለልዑል እግዚአብሔር ታማኝ አለመሆኔ
ነውና፣
ይህም ደግሞ የሚያስቀጣኝ በደል በሆነ
ነበር::

[29]"በጠላቴ ውድቀት ደስ ብሎኝ፣
በደረሰበትም መከራ ሐሤት አድርጌ
እንደ ሆነ፣
[30]እኔ ግን በነፍሱ ላይ ክፉ እንዲመጣ
በመራገም፣
አንደበቴን ለኀጢአት ከቶ አሳልፌ
አልሰጠሁም::
[31]የቤቴ ሰዎች፣ 'ከኢዮብ ከብት ሥጋ
አስቈርጦ፣
ያልጠገበ ማን ነው' ብለው ካልሆነ፣
[32]ነገር ግን ቤቴ ለመንገደኛው ዘወትር
ክፍት ስለ ነበር፣
መጻተኛው በጐዳና ላይ አያድርም ነበር::

31፥1 ዘፀ20፥14፡17፤ ዘዳ5፥18፤ምሳ4፥25፤ 17፥24፤ማቴ5፥28፤ 2ጴጥ2፥14
31፥2 ዘኍ26፥55፤ ኢዮ16፥19፤20፥29፤ መዝ11፥6፤16፥5፤50፥ 18፤መክ3፥22፤5፥19፤ 9፥9
31፥3 ኢዮ18፥12፤ 21፥30፤34፥22፤ሮሜ 2፥9
31፥4 ቍ14፤2ዜና 16፥9፤ኢዮ10፥4፤መዝ 139፥3፤ዳን4፥37፤5፥23
31፥5 ኢዮ15፥31
31፥6 ዘፍ6፥9፤ዘሌ 19፥36፤ኢዮ2፥3፤6፥2፤ 23፥10፤መዝ139፥23
31፥7 ኢዮ9፥30፤ 23፥11፤መዝ7፥3
31፥8 ቍ12፤ኢዮ 5፥5፤20፥10፤ሚክ 6፥15፤ዮሐ4፥37
31፥9 ዘዳ11፥16፤ኢ ዮ24፥15፤ምሳ5፥3፤7፥ 5፤ያዕ1፥14
31፥10 ዘዳ28፥30፤ መሳ16፥21
31፥11 ዘፍ38፥24፤ ዘፀ21፥12፤ምሳ6፥32- 33፤ዮሐ8፥4-5
31፥12 ቍ8፤ኢዮ 15፥30፤26፥6
31፥13 ዘፀ21፥2-11 ፤ዘሌ25፥39-46፤ዘዳ 5፥14፤24፥14-15
31፥14 ቍ4፡37፤ ኢዮ33፥5፤መዝ10፥ 13፡15፤94፥7፤ኢሳ10፥ 3፤ኤር5፥31፤ሆሴ9፥ 7፤ሚክ7፥4፤ቈላ4፥1
31፥15 ኢዮ4፥17፤ 10፥3፤ምሳ22፥2፤ኤፌ 6፥9
31፥16 ዘሌ25፥17፤ ኢዮ5፥16፤22፥7፡9፤ ያዕ1፥27
31፥17 ኢዮ6፥27፤ 22፥7
31፥18 ኢሳ51፥18
31፥19 ኢዮ22፥6፤ 24፥4፤ኢሳ58፥7
31፥20 መሳ6፥37፤ ኢዮ29፥13
31፥21 ኢዮ22፥7፤ 29፥7፡9፤ያዕ1፥27
31፥22 ዘኍ15፥30፤ ኢዮ5፥15፤38፥15፤ መዝ10፥15፤37፥17፤ 137፥5
31፥23 ዘፍ20፥11፤ ኢዮ10፥3፤13፥11፤ 30፥15

31፥24 ኢዮ22፥25፤ማቴ6፥24፤ሉቃ12፥15 31፥25 ዘፍ12፥16፤ ኢዮ22፥24፤መዝ49፥6፤52፥7፤62፥10፤ኢሳ10፥14፤ሕዝ28፥5፤ሉቃ 12፥20-21 31፥26 ዘፍ1፥16፤ኢዮ25፥5 31፥27 ዘዳ11፥16፤ኢዮ 24፥15፤ኤር8፥2፤16፥11፤ያዕ1፥14 31፥28 ዘፍ38፥24፤ዘኍ 11፥20፤ዘዳ17፥2-7፤ሕዝ8፥16 31፥29 ዘኍ14፥1፤መዝ35፥15፤ ምሳ17፥5፤24፥17-18፤አብ1፥12፤ማቴ5፥44 31፥30 ኢዮ5፥3፤ ሮሜ12፥14 31፥31 ኢዮ22፥7 31፥32 ዘፍ19፥2-3፤ መሳ19፥20፤ማቴ25፥35፤ሮሜ12፥13

[ሀ]12 *ዕብራይስጡ ለባዶን ይላል::*

*31፥4፤* ኤሊሁ በ34፥21 ላይ ደግሞታል::

31፥6 *እግዚአብሔር በእውነተኛ ሚዛን ይመዝነኝ፤* 6፥2፤ ምሳ 16፥12፤ 21፥2፤ 24፥12 ይመ:: *ነውር እንደሌለብኝም፤* ኀጢአት የሌለበት ፍጹም ሰው መሆኑን አያመለክትም (የ1፥1 ማብ *ይመ*)::

31፥12 *የሚያጠፋ፤* የ26፥6 ማብ *ይመ*::

*31፥13-23፤* ኢዮብ፣ ሰዎች እርስ በርሳቸው ሊኖራቸው ስለሚገባ ቅንነትና መተሳሰብ ትክክለኛውን ነገር ገልጾአል፤ ይኸውም የሰው አፈጣጠር ለእኩልነቱ መሠረት መሆኑን (ቍ 13-15)፣ ለተቸገሩት ርኅራኄ አስፈላጊ መሆኑን (ቍ 16-20)፣ ኀይልም ሆነ ሥልጣን በትክክል ሥራ ላይ መዋል እንዳለበትም (ቍ 21-23) አስተምሮአል::

31፥16-17 *ለድኻ... የመበለቲቱን፤* የ29፥12-13 ማብ *ይመ*::

*31፥24-28፤* ስስታምነትና (ቍ 24-25 )ጣዖትን ማምለክ (ቍ 26-27) ሁለቱም በእግዚአብሔር ዘንድ አስጸያፊዎች ናቸው (ቍ 8፤ ማቴ 6፥19-24፤ ቈላ 3፥5 *ይመ*)::

31፥25 *በባለጠግነቴም ብዛት፤* 1፥3፡10 *ይመ*::

*31፥26-27፤* ፀሓይና ጨረቃ መመለክ የለባቸውም (ዘዳ 4፥19፤ 17፥3፤ ሕዝ 8፥16-17 *ይመ*)::

31፥27 *ስሞ፤* በጥንት ጊዜ የአምልኮ መልክ ነበር (1ነገ 19፥18፤ ሆሴ 13፥2 *ይመ*)::

*31፥29-32፤* የጠላትን ሥቃይ አይቶ መደሰት በሙሴ ሕግ ተኰንኖአል (ዘፀ 23፥4-5)፤ ጌታ ኢየሱስም ኰንኖታል (ማቴ 5፥43-47)::

[33]ሰዎች[ӿ] እንደሚያደርጉት በደሌን በልቤ
በመሰወር፣
ኀጢአቴን ሸሽጌ ከሆነ፣
[34]ሕዝቡን በመፍራት፣
የወገኖቼንም ንቀት በመሸሽ፣
ወደ ደጅ ሳልወጣ፣ ዝም ብዬ ቤት
ውስጥ አልተቀመጥሁም::

[35]"ምነው የሚሰማኝ ባገኝ!
የመከላከያ ፊርማዬ እነሆ፤ ሁሉን
የሚችል አምላክ ይመልስልኝ፤
ከሳሼም ክሱን በጽሑፍ ያቅርብ::
[36]በእርግጥ ትከሻዬ ላይ በደረብሁት፣
እንደ አክሊልም ራሴ ላይ በደፋሁት
ነበር::
[37]እያንዳንዱን ርምጃዬን በገለጽሁለት፣
እንደ ልዑል እየተንጐራደድሁ
በቀረብሁት ነበር::

[38]"ዕርሻዬ በእኔ ላይ ጮኻ ከሆነ፣
ትልሞቿ ሁሉ በእንባ ርሰው እንደ ሆነ፣
[39]ፍሬዋን ያለ ዋጋ በልቼ፣
የባለመሬቶቿን ነፍስ አሳዝኜ ከሆነ፣
[40]በስንዴ ፈንታ እሾህ፣
በገብስም ምትክ ዐረም ይብቀልብኝ::"

የኢዮብ ቃል ተፈጸመ::

## ኤሊሁ

32 ኢዮብ በበኩሉ ራሱን እንደ ጻድቅ ቈጥሮ ስለ ነበር፣ እነዚህ ሦስት ሰዎች ለእርሱ መልስ መስጠታቸውን ተዉ:: [2]ከራም ወገን የሆነው፣ የቡዛዊው የባርክ ኤል ልጅ ኤሊሁ ግን ኢዮብ ከእግዚአብሔር ይልቅ ራሱን ጻድቅ ስላደረገ፣ እጅግ ተቈጣው:: [3]ሦስቱ የኢዮብ ጓደኞች በኢዮብ ላይ መፍረድ[ገ] እንጂ፣ ነገሩን ሊያሳምኑት ስላልቻሉ፣ በእነርሱም ላይ ተቈጣ:: [4]ኤሊሁ፣ ሌሎቹ በዕድሜ ይበልጡት ስለ ነበር ከእነ ርሱ ቀድሞ ለኢዮብ ሳይናገር ቈየ:: [5]ነገር ግን እነዚህ ሦስቱ የሚሉትን ባጡ ጊዜ ቍጣው ነደደ::
[6]ስለዚህ የቡዛዊው የባርክኤል ልጅ ኤሊሁ እንዲህ አለ፤

"እኔ በዕድሜ ታናሽ ነኝ፤
እናንተ ግን አዛውንቶች ናችሁ፤
ከዚህም የተነሣ የማውቀውን ለመናገር
አልደፈርሁም፤
ፈርቼ ዝም አልሁ::

[7]'ዕድሜ ይናገራል፤
ረጅም ዘመን ጥበብን ያስተምራል' ብዬ
ነበር::
[8]ነገር ግን በሰው ያለው መንፈስ፣
ሁሉን የሚችል አምላክ እስትንፋስ፣
ማስተዋልን ይሰጣል::
[9]ጠቢባን የሚሆኑት በዕድሜ የገፉ[ጠ] ብቻ
አይደሉም፤
የሚያስተውሉም ሽማግሌዎች ብቻ
አይደሉም::

[10]"ስለዚህ፣ 'ስሙኝ፣
እኔም የማውቀውን ልንገራችሁ'
እላለሁ::
[11]እናንተ በምትነጋገሩበት ጊዜ ታገሥሁ፤
ቃላት እየመረጣችሁ፣
ስትናገሩ በጥሞና ሰማኋችሁ፤
[12]በሙሉ ልብ አዳመጥኋችሁ፤
ነገር ግን ከእናንተ የኢዮብን ቃል
ያስተባበለ ማንም የለም፤
ለንግግሩም አጸፋ የመለስ አልተገኘም::
[13]'እኛ ጥበብ አግኝተናል፤
ሰው ሳይሆን እግዚአብሔር ይርታው'
አትበሉ::

31፥33 ዘፍ3፥8፤ መዝ32፥5፤ምሳ 28፥13
31፥34 ዘፀ23፥2፤ መዝ32፥3፤39፥2
31፥35 ኢዮ9፥24፤ 27፥7፤30፥28
31፥36 ዘፀ28፥12፤ ኢዮ29፥14
31፥37 ቍ14፤ኢዮ 11፥11፤21፥28
31፥38 ዘፍ4፥10፤ መዝ65፥10
31፥39 ዘሌ19፥13፤ 1ነገ21፥19፤ያዕ5፥4
31፥40 ዘፍ3፥18፤ መዝ72፥20፤ኤር5 1፥64፤ሰፎ2፥9፤ማቴ 13፥7:26
32፥1 ቍ15፤ኢዮ 2፥3፤10፥7
32፥2 ቍ1፤ዘፍ 22፥21፤ኢዮ13፥19፤ 27፥5፤30፥21፤35፥2
32፥3 ቍ12-13፤ ኢዮ15፥13፤42፥7
32፥4 ዘሌ19፥32
32፥6 ኢዮ15፥10
32፥7 1ዜና29፥15፤ 2ዜና10፥6
32፥8 ቍ18፤ኢዮ 12፥13፤27፥3፤መዝ 119፥34፤ያዕ1፥5
32፥9 ኢዮ12፥12: 20፤መዝ119፥100፤ ሉቃ2፥47፤1ቆሮ1፥26 ፤1ጢሞ4፥12
32፥10 ኢዮ5፥27፤ 33፥1:31:33፤34፥2: 16፤37፥2:14፤መዝ 34፥11
32፥12 ቍ3
32፥13 ኢዮ4፥12፤ 11፥5፤መክ9፥11

ӿ33 ወይም አዳም እንዳደረገው
ገ3 የማሶሬቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ ጥንታዊው የዕብራውያን ጸሐፍት ትውፊት ግን ኢዮብንም ሆነ እግዚአብሔርን ኰነኑ ይላል::
ጠ9 ወይም፣ ብዙ ወይም፣ ታላቅ

*31፥33-34፤* ግብዝነቱን በግልጽ ይክዳል::

31፥33 *ሰዎች እንደሚያደርጉት፤* አዳም እንዳደረገው ለማለት ነው (ዘፍ 3፥8-10፤ ሆሴ 6፥7 ይመ)::

*31፥35-37፤* ኢዮብ ለመጨረሻ ጊዜ "የፍትሕ ያለህ" በማለት ይጮኻል:: በእግዚአብሔር ፊት የገባውንም መሐላ በፊርማው ያረጋግጣል::

31፥35 *የሚሰማኝ፤* የ5፥1፤ 9፥33፤ 16፥18-21፤ 19፥25 ማብ ይመ:: *ሁሉን የሚችል አምላክ፤* የ38፥1 ማብ ይመ:: *ከሳሼም፤* በዕብራይስጡ "ሰይጣን" ከሚለው ጋር አንድ አይደለም (የ1፥6 ማብ ይመ):: እዚህ ላይ የኢዮብ ከሳሽ:- 1) ጠላቱ የሆነ ሰው ምናልባትም ከሦስቱ ወዳጆቹ አንዱ ወይም 2) ራሱ እግዚአብሔር ሊሆን ይችላል:: ኢዮብ በማንኛውም ሁኔታ ውስጥ በእግዚአብሔር የሚከሰስና እግዚአብሔርም የሚፈርድበት ይመስለዋል::

31፥36 *ትከሻዬ፤* ጠቀሜታቸውን ዘወትር ለማስታወስ ይቻል ዘንድ፣ ጽሑፎችን አንዳንድ ጊዜ በትከሻ ላይ መሸከም የተለመደ ነበር (ዘፀ 28፥12 ይመ)::

*31፥38-40፤* ከዚህ በፊት የነበረውን ዋና ሐሳብ የሚያጠቃልል ከፍተኛ መሐላ እንዲሁም ልዩ አጽንዖት የሚሰጥ ነው፤ ኢዮብ ለማኅበረ ሰቡ ፍትሕ ራሱን ያላስገዛ ከሆነ ምድሩን ይረግማል (እንዲሁም 13-15 ይመ)::

31፥40 *የኢዮብ ቃል ተፈጸመ፤* የኢዮብ ክርክርና ቅሬታ እዚህ ላይ ያበቃል:: ከመለኮታዊ ንግግር በኋላ ግን ስለ ኀጢአቱ በጥልቅ ማዘኑን ይገልጻል (40፥4-5፤ 42፥2-6)::

*32፥1-37፤* አራተኛው የኢዮብ ወዳጅ ኤሊሁ ነው፤ ዕድሜው ከሦስቱ የኢዮብ ወዳጆች ያንሳል (32፥4:6-7:9)፤ እርሱም ለታላላቆቹ አክብሮት በመስጠት ክርክራቸውን ቆሞ ያዳምጥ ነበር:: አሁን ግን ኢዮብና ሦስቱ ወዳጆቹ የተሳሳቱ መሆናቸውን ለማሳየት መዘጋጀቱን ይናገራል:: የመጽሐፈ ኢዮብ ጸሓፊ ለአራቱም የኤሊሁ ግጥሞች (32፥5-33፤ 34፤ 35፤ 36-37)፣ ለእያንዳንዳቸው በስድ ንባብ መግቢያ ጽፎላቸዋል::

32፥1 *ራሱን እንደ ጻድቅ ቈጥሮ ስለ ነበር፤* ኢዮብ መከራ ቢበዛበትም ቅንነቱን ደጋግሞ ይናገር ነበር::

32፥2-3 *ተቈጣው፤* ኢዮብ በደል የሌለበት መሆኑን በአጽንዖት መግለጹ ዞሮ ዞሮ እግዚአብሔርን ተወቃሽ የሚያደርግ ስለመሰለው፣ ኤሊሁ ይህንን አልወደደውም፤ የኢዮብ ወዳጆች የኢዮብን በደል የለብኝም ባይነት ውድቅ ለማድረግ አለመቻላቸውም፣ እግዚአብሔርን ተወቃሽ የሚያደርግ ስለሆነ እነርሱ ራሳቸው ትክክል አለመሆናቸውን ኤሊሁ ያምናል::

32፥2 *የቡዛዊው፤* በምሥራቅ በኩል የሚገኝ የቡዝ በረሓ ተወላጅ ነው (ኤር 25፥23 ይመ)::

32፥6:10:17፤ *የማውቀውን ለመናገር፤* ኤሊሁ የሚያውቀውን ለማካፈል ጉጉት አለው፤ ይህንም በብቃት ለማስተላለፍ ችሎታ ያለው መሆኑን ያምናል (የ36፥4 ማብ ይመ)::

32፥6 *ታናሽ... አልደፈርሁም፤* ኤር 1፥6-8፤ 1ጢሞ 4፥12፤ 2ጢሞ 1፥7 ይመ::

32፥8 *ሁሉን የሚችል አምላክ እስትንፋስ፤* 33፥4 ይመ::

[14]ኢዮብ ግን ቃሉን በእኔ ላይ አልሰነዘረም፤
እኔም እንደ እናንተ አነጋገር መልስ
አልሰጠውም።
[15]"እነርሱ ተስፋ ቈርጠው፣ የሚሉት
የላቸውም፤
የሚናገሩትም ጠፍቶአቸዋል።
[16]እንግዲህ እነርሱ መልስ ሳጡ፣
ጸጥ ብለውም ስለ ቆሙ፣ በትዕግሥት
ልጠብቅን?
[17]እኔም የምለው ይኖረኛል፤
የማውቀውንም እገልጣለሁ።
[18]የምናገረው ሞልቶኛልና፤
በውስጤ ያለውም መንፈስ ገፋፍቶኛል።
[19]ውስጤ እንደ ተከደነና መተንፈሻ እንዳጣ
የወይን ጠጅ፣
ሊፈነዳ እንደ ተቃረበም አዲስ የወይን
ጠጅ አቁማዳ ሆኖአል።
[20]ተናግሬ መተንፈስ አለብኝ፤
አፌንም ከፍቼ መልስ መስጠት
ይገባኛል።
[21]ለማንም አላደላም፤
ሰውንም አላቈላምጥም።
[22]ማቈላመጥን ባውቅበትማ ኖሮ፣
ፈጣሪዬ ፈጥኖ ባጠፋኝ ነበር።

33 "አሁን ግን ኢዮብ ሆይ፣ ንግግሬን
ስማ፤
የምለውንም ሁሉ አድምጥ።
[2]እንግዲህ አፌን እከፍታለሁ፤
አንደበቴም ይናገራል።
[3]ቃሌ ከቅን ልብ ይወጣል፤
ከንፈሬም የማውቀውን በትክክል ይናገራል።
[4]የእግዚአብሔር መንፈስ ፈጥሮኛል፤
ሁሉን የሚችለውም አምላክ
እስትንፋስ ሕይወት ሰጥቶኛል።
[5]የምትችል ከሆነ መልስልኝ፤
ተዘጋጅተህም በፊቴ ቁም።
[6]በእግዚአብሔር ፊት እኔም እንዳንተው ነኝ፤
የተፈጠርሁትም ደግሞ ከዐፈር ነው።
[7]እኔን መፍራት የለብህም፤
እጄም ሊከብድብህ አይገባም።
[8]"በእርግጥ የተናገርኸውን ሰምቻለሁ፤
እንዲህም ስትል አድምጫለሁ፤
[9]'ኀጢአት የሌለብኝ ንጹሕ ነኝ፤
ከበደል ነጻ ነኝ፤ እድፈትም የለብኝም፤
[10]እግዚአብሔር ግን ሰበብ ፈልጎብኛል፤
እንደ ጠላቱም ቈጥሮኛል፤
[11]እግሬን በግንድ አጣብቆአል፤
እንቅስቃሴዬንም ሁሉ ይከታተላል።'
[12]"ነገር ግን እግዚአብሔር ከሰው ስለሚበልጥ፣
ትክክል እንዳልሆንህ እነግርሃለሁ።
[13]የሰውን አቤቱታ[a] እንደማይሰማ፣
ለምን ታማርርበታለህ?
[14]ሰው ባያስተውለውም፣
እግዚአብሔር በተለያየ መንገድ ይናገራል፤
[15]ሰዎች ዐልጋቸው ላይ ተኝተው ሳሉ፣
ከባድ እንቅልፍ ሲወድቅባቸው፣
በሕልም፣ በሌሊትም ራእይ፣ ይናገራል።

32፥14 ኢዮ23፥4
32፥15 ቍ1
32፥17 ኢዮ5፥27፤ 33፥3፤36፥4
32፥18 ቍ8፤ሐሥ 4፥20፤1ቆሮ9፥16፤ 2ቆሮ5፥14
32፥19 ኤር20፥9፤ አሞ3፥8፤ማቴ9፥17
32፥20 ኢዮ4፥2፤ ኤር6፥11
32፥21 ዘሌ19፥15፤ 2ዜና19፥7፤ኢዮ13፥10፤ምሳ29፥5፤ማቴ 22፥16፤1ተሰ2፥5
32፥22 ኢዮ4፥17፤ 9፥9፤መዝ12፥2-4
33፥1 ኢዮ6፥28፤ 13፥6፤32፥10
33፥3 1ነገ3፥6፤ኢዮ 6፥28፤መዝ7፥10፤11፥2፤64፥10
33፥4 ዘፍ1፥2፤ዘኍ 16፥22፤ኢዮ10፥3፤ 12፥10፤27፥3
33፥5 ቍ32፤ኢዮ 13፥18፤31፥14
33፥6 ኢዮ4፥19፤ ሐሥ14፥15፤ያዕ5፥17
33፥7 ኢዮ9፥34፤ 2ቆሮ2፥4
33፥9 ኢዮ2፥9፤9፥ 30፤10፥7፤13፥23
33፥10 ኢዮ13፥24
33፥11 ኢዮ13፥27፤ 14፥16፤ምሳ3፥6፤ ኢሳ30፥21
33፥12 ኢዮ5፥9፤ መዝ8፥4፤50፥21፤መክ 7፥20፤ኢሳ55፥8-9
33፥13 ኢዮ11፥8፤ 40፥2፤ኢሳ45፥9 33፥14 ቍ29፤ኢዮ4፥12፤መዝ62፥11 33፥15 ዘፍ2፥21፤15፥1፤20፥3፤ኢዮ4፥13፤ዳን2፥19፤ማቴ27፥19፤ሐሥ16፥9

[a] 13 ወይም፣ ለምንገሩ ምንም እንደማይመልስ

32፥14 *እኔም እንደ እናንተ አነጋገር መልስ አልሰጠውም፤* ዐቢይ ነገር መዘለሉ ኤሊሁ ይሰማዋል፤ በዕድሜ ብዛት የሚገኝ ዕውቀት ባልሠራበት ጊዜ የእግዚአብሔር መንፈስ እውነተኛውን ነገር ይገልጣል።

*32፥15-22፤* ኤሊሁ ከራሱ ጋር ይነጋገራል፤ የሚናገረው ግን ለሚሰሙት ሁሉ የሚጠቅም ነው።

32፥15-16 *የሚናገሩትም ጠፍቶአቸዋል... መልስ ሳጡ፤* ቍ 5 ይመ። ሦስተኛው ዙር ክርክር መቋረጡ የበልዳዶስን የመጨረሻ ንግግር በአጭር አስቀርቶታል፤ ሶፋርም ሦስተኛ ዙር ንግግር እንዳያደርግ አግዶታል (የ22፥1-26፥14 ማብ ይመ)።

32፥18 *የምናገረው ሞልቶኛልና፤* የኤሊሁ ንግግር እስከ ም 37 ድረስ ሳይቋረጥ ይቀጥላል፤ ኢዮብ የገጠመው ችግር መፍትሔ ያገኘ ዘንድ ኤሊሁ የሚያቀርበው መፍትሔ አለው። ከዚሁም ጋር የቀደመውን የኢዮብን ሕይወት መሠረት ያደረገ ነው ተብሎ የተሰነዘረውን ወቀሳ ኤሊሁ አሜን ብሎ አይቀበልም፤ የእርሱ ወቀሳ መሠረት ያደረገው ግን የራሱን የኢዮብን ጥቅስ ነው። በመጨረሻው ክፍል እግዚአብሔር ኤሊሁን ከሌሎች የኢዮብ ወዳጆች ጋር ያላወገዘውም ከዚህ የተነሣ ነው (42፥7 ይመ)።

32፥19 *ሊፈነዳ እንደ ተቃረበም አዲስ የወይን ጠጅ አቁማዳ፤* አሮጌ አቍማዳ በቀላሉ ሊተረተር ወይም ሊፈነዳ ይችላል (ማቴ 9፥17 ይመ)፤ አዲሱ ግን እንዲህ አይደለም፤ ኤሊሁም ለመናገር ፈልጉአል።

*33፥1-33፤* አሁን ኤሊሁ ወደ ኢዮብ በመመለስ፣ ኢዮብን በቀጥታ ያናግረዋል፤ ኢዮብን በስሙ ጠርቶ ማናገሩም (ቍ 1፥31፤ 37፥14 ይመ) ከሦስቱ የኢዮብ ወዳጆች ልዩ ያደርገዋል።

33፥1 *የምለውንም ሁሉ አድምጥ፤* ኤሊሁ አሁን የሚሰጠው ምክር ምን ያህል አስፈላጊና ጥበብም የተሞላበት መሆኑን በርግጠኝነት ያምናል (31፡33 ይመ)።

33፥4 *የእግዚአብሔር መንፈስ ፈጥሮኛል፤* ዘፍ1፥2 እና ማብ ይመ። *ሁሉን የሚችለውም አምላክ እስትንፋስ፤* 32፥8 ይመ። *ሕይወት ሰጥቶኛል፤* 37፥3፤ እንዲሁም ዘፍ 2፥7 እና ማብ ይመ።

33፥5 *መልስልኝ፤* ኤሊሁ ንግግሩን ተመሳሳይ በሆነ መልክ ጀምሮ በዚሁ ይጨርሳል (ቍ 35 ይመ)። *የምትችል ከሆነ፤* የበላይ የመሆን ባሕርዩን ያሳያል።

33፥6 *የተፈጠርሁትም ደግሞ ከዐፈር ነው፤* የ4፥19 ማብ ይመ።

33፥7 *እጄም ሊከብድብህ አይገባም፤* በሌላ ቦታ ይህ ፈሊጣዊ ንግግር የገባው ለእግዚአብሔር ብቻ ነው (23፥2 እና የ1ሳሙ 5፥6 ማብ ይመ)።

33፥8 *በእርግጥ የተናገርኸውን፤* የኤሊሁ የክርክር ዘዴ ኢዮብ የተናገረውን በመጥቀስ (ቍ 9-11፤ 34፥5-6፥9፤ 35፥2-3)፣ የትላይና እንዴት እንደ ተሳሳተ ማሳየት ነው። ጥቅሶቹ ምንጊዜም ቃል በቃል የተጠቀሱ ሳይሆኑ ይቻላሉ፤ ይህም የኤሊሁ ዐላማ የኢዮብን መከራከሪያ ዋና ሐሳብ ልብ በማለት ክርክሩን መቀጠል መሆኑን ያመለክታል።

*33፥11፤* እዚህ ላይ ኤሊሁ የኢዮብን ንግግር ይደግመዋል (13፥27 ይመ)።

33፥12 *ትክክል እንዳልሆንህ፤* ኢዮብ መታረም ያለበት መሆኑን ኤሊሁ ያምናል፤ ኢዮብ እግዚአብሔርን እንደ ጠላቱ አድርጎ መቍጠሩ (10፤ 13፥24፤ 19፥11 ይመ)፣ ያለጥርጥር ስሕተት ነው፤ ኢዮብ በደል የለብኝም ማለቱም (ቍ 9)፣ ኤሊሁን አስቈጥቶታል፤ ይሁን እንጂ ኢዮብ፣ ንጹሕ ነኝ ኀጢአትም የለብኝም ብሎ አያውቅም፤ ያሰማቸው እንዳንድ ቃላት በኤልፋዝም ሳይቀር ነገሩ በዚህ መልክ ቢተረጐምም እንኳ (15፥14-16 ይመ)፣ ዘግናኝ ለሆነ በደል ተገቢ የሆነውን ቅጣት በመቀበሉ፣ "ይህ ከቶ በእኔ ላይ እንዲደርስ ተገቢ ነውን?" ቢልም እንኳ፣ ኢዮብ ኀጢአተኛ መሆኑን ያምናል (7፥21፤ 13፥26)። እግዚአብሔር ዝም ብሎአል በማለት ኢዮብ ቅሬታ ማሰማቱ (ቍ 13 ይመ)፣ ኤሊሁን አስከፍቶታል። ከዚሁም ጋር፣ "እግዚአብሔር ሰውን ማናገር ትቶአል" ለሚለው አጠቃላይና ድፍን ያለ ሐሳብ ኤሊሁ ተጠያቂ ያደረገው ኢዮብን ነው፤ ይሁን እንጂ ኢዮብ የገለጸው አሁን ባለበት አሠቃቂ ሁኔታ እግዚአብሔር ዝም ያለው መሆኑን ነው።

33፥15 *ሰዎች ዐልጋቸው ላይ ተኝተው ሳሉ... በሕልም፤* ኤሊሁ እዚህ የኤልፋዝን ንግግር ይደግመዋል (4፥13 ይመ)።

[16]በጆሮቻቸው ይናገራል፤
በማስጠንቀቂያም ያስደነግጣቸዋል፤
[17]ሰውን ከክፉ ሥራው ይመልሳል፤
ከትዕቢት ይጠብቃል፤
[18]ነፍሱን ከጕድጓድ፣[a]
ሕይወቱንም ከሰይፍ[b] ጥፋት ያድናል።
[19]ደግሞም ሰው ታሞ በዐልጋው ላይ ሳለ፣
በዐጥንቱ የዘወትር ሥቃይ ይገሥጸዋል፤
[20]ያኔም ሕይወቱ መብልን ትጠላለች፤
ነፍሱም ምርጥ ምግብን ትጠየፋለች።
[21]እንዳልነበረ ሆኖ ሥጋው ይመነምናል፤
ተሸፍኖ የነበረው ዐጥንቱም ገጦ ይወጣል።
[22]ነፍሱ ወደ ጕድጓድ፣[c]
ሕይወቱም ወደ ሞት[d] መልእክተኞች ትቀርባለች።

[23]"ሆኖም ትክክለኛውን መንገድ ለሰው ያመለክት ዘንድ፣
መካከለኛም ይሆንለት ዘንድ፣
ከሺህ አንድ መልአክ ቢገኝ፣
[24]ለሰውየውም በመራራት፣
'ቤዛ አግኝቼለታለሁና፣
ወደ ጕድጓድ[e] እንዳይወርድ አድነው'
ቢለው፣
[25]በዚህ ጊዜ ሥጋው እንደ ሕፃን ልጅ ገላ ይታደሳል፤
ወደ ወጣትነቱም ዘመን ይመለሳል።
[26]ወደ እግዚአብሔር ይጸልያል፤ ሞገስም ያገኛል፤
የእግዚአብሔርን ፊት ያያል፤ ሐሤትም ያደርጋል፤
እግዚአብሔር ወደ ጽድቅ ቦታው ይመልሰዋል።
[27]ከዚያም ወደ ሰዎች መጥቶ እንዲህ ይላል፤
'ኀጢአትን ሠርቻለሁ፤ ትክክል የሆነውን አጣምሜአለሁ፤
ነገር ግን የእጄን አላገኘሁም።
[28]ነፍሴ ወደ ጕድጓድ[f] እንዳትወርድ፣
ታድጎአታል፤
በሕይወትም ሆኜ ብርሃን አያለሁ።'
[29]"እግዚአብሔር ይህን ሁሉ፣
ሁለት ሦስት ጊዜ ለሰው ያደርጋል።
[30]ይኸውም የሕይወት ብርሃን ይበራለት ዘንድ፣
ነፍሱን ከጕድጓድ[g] ለመመለስ ነው።
[31]"ኢዮብ ሆይ፤ ልብ ብለህ ስማኝ፤
እኔ ልናገር፤ አንተ ዝም በል።
[32]የምትለው ካለህ፣ መልስ ስጠኝ፤
ትክክለኛነትህንም ማወቅ እፈልጋለሁና ተናገር፤
[33]አለበለዚያ፣ ዝም ብለህ ስማኝ፤
እኔም ጥበብን አስተምርሃለሁ።"

# 34

ኤሊሁ በመቀጠል እንዲህ አለ፤
[2]"እናንት ጠቢባን፣ ቃሌን ስሙ፤
ዐዋቂዎችም አድምጡኝ።
[3]ምላስ ምግብን አጣጥሞ እንደሚለይ፣
ጆሮም የንግግርን ለዛ ለይቶ ያውቃል።

33፥16 ኢዮ6፥4፤ 36፥10፡15፤መዝ88፥15፡16 33፥17 ኢዮ20፥6 33፥18 ቍ22፡24፡28፡30፤ኢዮ15፥22፤ መዝ28፥1፤30፥9፤69፥15፤88፥6፤103፥4፤ምሳ 1፥12፤ኢሳ14፥15፤ 38፥17፤ዮና2፥6፤ዘካ9፥11፤ማቴ26፥52 33፥19 ዘፍ17፥1፤ ዘዳ8፥5፤ኢዮ5፥17፤ 16፥16፤መዝ6፥2፤38፥3፤ኢሳ38፥13፤2ቆሮ 12፥7-10፤ያዕ1፥3 33፥20 ኢዮ3፥24፤ 6፥6፤መዝ102፥4፤ 107፥18 33፥21 ኢዮ2፥5፤ 16፥8 33፥22 ቍ18፤ኢዮ 38፥17፤መዝ9፥13፤88፥3፤107፥18፤116፥3 33፥23 ኢዮ36፥9-10፤ሚክ6፥8፤ገላ3፥19፤ዕብ8፥6፤9፥15 33፥24 ቍ18፤ኢዮ 6፥22 33፥25 2ነገ5፥14፤ መዝ103፥5 33፥26 ዕዝ3፥13፤ ኢዮ5፥15፤22፥26፤ መዝ13፥5፤50፥15፤51፥12፤ምሳ8፥35፤12፥21 18፥22፤ሉቃ2፥52፤ 1ዮሐ1፥9 33፥27 ዘኍ22፥34፤ዕዝ9፥13፤ መዝ22፥27፤51፥13፤ ሉቃ15፥21፤ሮሜ 6፥21፤ያዕ2፥13 33፥28 ቍ18፤ዘፀ 15፥13፤ኢዮ17፥16፤ 22፥28፤መዝ34፥22፤ 107፥20 33፥29 ቍ14፤መዝ 139፥16፤ምሳ16፥9፤ 20፥24፤ኤር10፥23፤1ቆሮ12፥6፤ኤፌ1፥11፤ፊል2፥13 33፥30 ቍ18፤መዝ49፥19፤56፥13፤116፥9፤ኢሳ53፥11፤60፥1፤ኤፌ5፥14፤ ያዕ5፥19 33፥31 ቍ33፤ኢዮ32፥10፤ኤር23፥18 33፥32 ቍ5፤ ኢዮ6፥29፤35፥2 33፥33 ቍ31፤ኢዮ6፥24፤32፥10፤ምሳ10፥8፡10፡ 19 34፥2 ኢዮ32፥10 34፥3 ኢዮ12፥11

[a]18 ወይም፣ *ነፍሱን ከመቃብር*
[b]18 ወይም፣ *ወንዝን ከመሻገር*
[c]22 ወይም፣ *ነፍሱ ወደ ሞት*
[d]22 ወይም፣ *ወደ ሙታን*
[e]24 ወይም፣ *ወደ መቃብር*
[f]28 ወይም፣ *ወደ መቃብር እንዳልሄድ ታድጎኛል*
[g]30 ወይም፣ *ነፍሱን ከሞት ለመመለስ ነው*

33፥18 *ከጕድጓድ፤* ቍ 22፡24፡28፡30 ይመ። በዳዊት መዝሙር ተደጋግሞ እንደተጠቀሰው በተምሳሌት መቃብርን የሚገልጽ ቃል ነው። *ከሰይፍ ጥፋት ያድናል፤* 36፥12 ይመ። በተምሳሌት መልክ በሕያዋንና በሙታን ዓለም መካከል ያለውን ድሬት የሚያሳይ ነው። "ሺላ" የሚለው የዕብራይስጥ ቃል፣ "ወንዝ"፣ "መላክ" እንዲሁም "የውሃ ቦይ" (ነህ 3፥15 ይመ) የሚል ትርጒም አለው። ስለዚህ "ወንዙ" በዘይቤያዊ አገላለጽ በዚህ ዓለምና በሚመጣው ዓለም መካከል ያለውን ጉዳና ያመለክታል።

33፥19 *ደግሞም ሰው ታሞ በዐልጋው ላይ፤* እግዚአብሔር የሚናገረው በሕልምና በራእይ ብቻ (ቍ 15 ይመ) አይደለም፤ እኛ ልናስተውለው በማንችለው መንገድ ሊናገር ይችላል (ቍ 14)። ኤሊሁ፣ ሰው ከኀጢአቱ ይመለስ ዘንድ እግዚአብሔር ያናግረዋል ማለቱ ትክክል ነው፤ ነገር ግን ኢዮብ ምን በደል እንደ ፈጸመ ያውቅ ዘንድ የእግዚአብሔርን ድምፅ መሻቱን ኤሊሁ በትክክል አልተረዳለትም (13፥22-23 ይመ)።

*33፥23-28፤* ቀደም ሲል ኤልፋዝ በአጭሩ እንደ ጠቀሰው (5፥17 ይመ)፣ ኤሊሁም ለቅጣት የሚመጣ መከራ ያለውን ጥቅም በአጽናዖት ከገለጸ በኋላ በማማለድ ላይ ስለ ተመሠረተው መዳን ይናገራል (የ5፥1 ማብ ይመ)። እግዚአብሔር በሙሉ ልብ ንስሓ የሚገቡትን፣ ከምሕረቱ የተነሣ ይቅር እንደሚላቸውም ተናግሮ አል (ቍ 27-28)። ይሁን እንጂ ኢዮብ ከእግዚአብሔር ጋር ያለውን ግንኙነት ኤሊሁ አሁንም አያውቅም፤ ይህን ምስጢር የሚያውቀው እግዚአብሔር ብቻ ነው (ም 1-2)።

33፥24 *ወደ ጕድጓድ እንዳይወርድ አድነው፤* ኢሳ 38፥17 ይመ። *ቤዛ፤* መዝ 49፥7-9ንና ማብ ይመ።

33፥25 *ሥጋው እንደ ሕፃን ልጅ ገላ ይታደሳል፤* በ2ነገ 5፥14 ላይ ከለምፅ ስለ መፈወስ ከተጠቀሰው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይ አገላለጽ ነው።

33፥26 *የእግዚአብሔርን ፊት ያያል፤* ቃል በቃል ትርጒሙ ሊታይ አይገባም (የዘፍ 16፥13 ማብ ይመ)።

33፥29 *ሁለት ሦስት ጊዜ፤* የ5፥19 ማብ ይመ።

33፥30 *ነፍሱን ከጕድጓድ ለመመለስ፤* እግዚአብሔር ሰውን ሲቀጣ ርኅራኄ የሌለው መስሎ ይታይ እንጂ ቅጣቱ ከፍቅር የተነሣ መሆኑን ኤሊሁ ያስተምራል፤ ሰው በዚህ ዓለም ሲኖር መቀበል የሚገባውን ተገቢውን ቅጣት አያገኝምና (ቍ 27)። *የሕይወት ብርሃን፤* የተስተካከለ መንፈሳዊ ሕይወት ማለት ነው (መዝ 27፥1፤ 49፥19 እና ማብ ይመ)። በአንዳንድ ዐውድ ላይ ሐሪት ትንሣኤን ያመለክታል (ኢሳ 53፥11 እና ማብ ይመ)።

33፥32 *ትክክለኛነትህንም ማወቅ እፈልጋለሁና፤* ይህ ሊሆን የሚችለው ኢዮብ ንስሓ ሲገባ ብቻ መሆኑን ኤሊሁ በአጽንዖት ይናገራል።

*34፥1-37፤* ከአራቱ የኤሊሁ ንግግሮች ይህኛው ሁለተኛው ሲሆን (የ32፥1-37፥24 ማብ ይመ)፣ በሦስት ክፍል የተመደበ ነው፤ 1) ለጠቢባን የቀረበ ነው (ቍ 2-15)፤ ይኸውም ያለጥርጥር ለሦስቱ ወዳጆች ነው፤ 2) ለኢዮብ ተብሎ የቀረበ ነው (ቍ 16-33)፤ 3) በ32፥15-22 (በዚያ ላይ የሚገኘውን ማብ ይመ) ላይ እንደ ተጠቀሰው ለራሱ የቀረበ ነው (ቍ 34-37)።

34፥2፡10 *አድምጡኝ (ስሙኝ)፤* ኤሊሁ በራሱ ጥበብ ከልክ በላይ የተመሰጠ ቢሆንም እንኳ፣ በቍ 4 ላይ በተመለከተው ትሑት ሁኔታው አንጻር ሲታይ ራሱን የእግዚአብሔር መልእክተኛ አድርጎ ሳይቈጥር አልቀረም (32፥8፡18 ይመ)።

34፥2 *ጠቢባን... ዐዋቂዎችም፤* "አስተዋዮችም" ተብሎአል (ቍ 10፡34)።

*34፥3፤* ኤሊሁ በ12፥11 ላይ የሚገኘውን የኢዮብን ቃል ከዚህ ላይ ይደግመዋል (የዚህኑ ማብ ይመ)።

[4]የሚበጀንን እንምረጥ፤
መልካሙንም አብረን እንወቅ።

[5]"ኢዮብ እንዲህ ይላል፤ 'እኔ ንጹሕ ነኝ፤
እግዚአብሔር ግን ፍትሕ ነሣኝ፤
[6]እውነተኛ ብሆንም፣
እንደ ውሸታም ተቈጥሬአለሁ፤
በደል ባይኖርብኝም፣
በማይፈወስ ቍስል ተመትቻለሁ።'
[7]ፌዝን እንደ ውሃ የሚጠጣት፣
እንደ ኢዮብ ያለ ሰው ማን ነው?
[8]ከክፉ አድራጊዎች ጋር ይተባበራል፤
ከኀጢአተኞችም ጋር ግንባር ይፈጥራል።
[9]'እግዚአብሔርን ለማስደሰት መሞከር፣
ለሰው አንዳች አይጠቅምም' ብሎአልና።

[10]"ስለዚህ፣ እናንተ አስተዋዮች ስሙኝ፤
ክፋትን ማድረግ ከእግዚአብሔር ዘንድ፣
በደልንም መፈጸም ሁሉን ከሚችል
አምላክ ይራቅ።
[11]ለሰው እንደ ሥራው ይመልስለታል፤
እንደ አካሄዱም ይከፍለዋል።
[12]በእውነት እግዚአብሔር ክፋትን አይሠራም፤
ሁሉን የሚችል አምላክ ፍትሕን
አያጣምምም።
[13]ምድርን እንዲገዛ የሾመው አለን?
የዓለምስ ሁሉ ባለቤት ያደረገው ማን ነው?
[14]እርሱ መንፈሱን መልሶ ቢወስድ፣
እስትንፋሱንም ወደ ራሱ ቢሰበስብ፣
[15]ሥጋ ለባሽ ሁሉ በአንድነት በጠፋ፣
ሰውም ወደ ዐፈር በተመለሰ ነበር።

[16]"ማስተዋል ካለህ ይህን ስማ፤
እኔ የምለውንም አድምጥ።
[17]ፍትሕን የሚጠላ ሊያስተዳድር ይችላልን?
አንተስ ጻድቁንና ኀያል የሆነውን
ትኰንናለህ?
[18]ነገሥታትን 'የማትረቡ ናችሁ፣'
መኳንንትንም፣ 'ክፉዎች ናችሁ'
የሚላቸው እርሱ አይደለምን?
[19]ሁሉም የእጁ ሥራ ስለ ሆኑ፣
እርሱ ለገዦች አያደላም፤
ባለጠጋውንም ከድኻው አብልጦ
አይመለከትም።
[20]እነርሱም እኩለ ሌሊት ላይ በድንገት
ይሞታሉ፤
ሕዝብ ተንቀጥቅጦ ሕይወቱ ያልፋል፤
ኀያላኑም የሰው እጅ ሳይነካቸው
ይወገዳሉ።

[21]"ዐይኖቹ የሰውን አካሄድ ይመለከታሉ፤
ርምጃውንም ሁሉ ይከታተላሉ።
[22]ክፉ አድራጊዎች የሚደበቁበት፣
ጨለማ ስፍራ ወይም የሞት ጥላ የለም።
[23]ሰው ለፍርድ ፊቱ ይቀርብ ዘንድ፣
እግዚአብሔር ቀጠሮ አይዝለትም።
[24]ያለ ምንም ጥያቄ ኀያላንን
ያንኰታኵታል፤
ሌሎችንም በቦታቸው ይሾማል።
[25]እርሱ ሥራቸውን ሁሉ ስለሚያውቅ፣
በሌሊት ይገለብጣቸዋል፤
እነርሱም ይደቃሉ።
[26]ስለ ክፋታቸውም፣
በሰው ሁሉ ፊት ይቀጣቸዋል፤
[27]እርሱን ከመከተል ተመልሰዋልና፤
መንገዱንም ችላ ብለዋል።
[28]የድኾች ልቅሶ ወደ እርሱ እንዲደርስ
ሰበብ ሆኑ፤
የመከረኞችን ጩኸት ሰማ።
[29]እርሱ ዝም ቢል፣ ማን ሊወቅሰው
ይችላል?

34፥4 ኢዮ12፥12፤ 1ተሰ5፥21፤ዕብ5፥14 34፥5 ኢዮ6፥29፤ 10፥7 34፥6 ኢዮ6፥4፡28፤ 9፥21፤10፥3፤ኢር10፥19 34፥7 ኢዮ9፥21፤ 15፥16 34፥8 ኢዮ22፥15 34፥9 ኢዮ9፥29-31፤21፥15 34፥10 ቍ12፡16፤ ዘፍ18፥25፤ዘዳ32፥4፤ ኢዮ8፥3፤12፥12፤32፥10፥36፥23፤መዝ92፥15፤ሮሜ3፥5፤9፥14 34፥11 ኢዮ21፥31፤ ኢር17፥10፤32፥19፤ሕዝ33፥20፤ማቴ16፥27 34፥12 ቍ10፤ኢዮ8፥3፤መዝ9፥16፤ቈላ3፥25፤2ተሰ1፥6፤ቲቶ1፥2፤ዕብ6፥18 34፥13 ኢዮ36፥23፤ 38፥4፡6፤ኢሳ40፥14፤ ዕብ1፥2 34፥14 ዘፍ6፥3፤ ዘኍ16፥22፤ኢዮ27፥3 34፥15 ዘፍ2፥7፤6፥13፤ኢዮ7፥21፤9፥22፤ መዝ90፥10፤ሰቆ3፥22፤ሚል3፥6፤ዮሐ3፥16 34፥16 ቍ10፤ኢዮ32፥10 34፥17 ቍ29፡30፤ 2ሳሙ23፥3-4፤ኢዮ10፥7፤40፥8፤ምሳ20፥8፡26፤24፥23-25፤28፥28፤ሮሜ3፥5-6 34፥18 ዘፀ22፥28፤ ኢዮ12፥18፤ኢሳ40፥24 34፥19 ዘሌ19፥15፤ ኢዮ10፥3፤13፥10፤ ሐሥ10፥34፤ያዕ2፥5 34፥20 ቍ25፤ዘፀ11፥4፤ኢዮ12፥19፤ 20፥8 34፥21 ኢዮ14፥16፤ ምሳ15፥3፤ኤር32፥19 ፤ዕብ4፥13 34፥22 ዘፍ3፥8፤ኢዮ3፥5፤11፥20፤መዝ74፥20 34፥23 ኢዮ11፥11፤መዝ11፥4 34፥24 ኢዮ12፥19፤ኢሳ8፥9፤9፥4፤ኤር51፥20፤ዳን2፥21፡34 34፥25 ቍ20፤ኢዮ11፥11፤ምሳ5፥21-23 34፥26 ዘፍ6፥5፤ኢዮ8፥22፤28፥24፤መዝ9፥5፤ኤር44፥5 34፥27 1ሳሙ15፥11፤መዝ14፥3 34፥28 ዘፀ22፥23፤ኢዮ5፥15፤12፥19 34፥29 ቍ17፤መዝ13፥1፡28፥1፤83፥1፡18፤97፥9፤109፥1፤ሮሜ8፥34

34፥5፡9 *ኢዮብ… ይላል… ብሎአልና፤* ኤሊሁ እንደ ገና የኢዮብን ቃል ይጠቅሳል፤ ከዚያም ከተዛባው ከኢዮብ ትምህርተ መለኮት አኳያ ለእግዚአብሔር ጽድቅ ጥብቅና ይቆማል (ለምሳሌ 9፥14-24፤ 16፥11-17፤ 19፥7፤ 21፥17-18፤ 24፥1-12፤ 27፥2 ይመ)፤ በቍ 5 ላይ የተጠቀሰው ዋና ሐሳብ ትክክል ነው (ከ 12፥4፤ ከ13፥18፤ ከ27፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። ኢዮብ ከበደል ፈጽሞ ነጻ ነኝ ያለበት ሁኔታ ባይኖርም፣ በቍ 6 ላይ ያለውም ሚዛናዊ በሆነ መልክ የኢዮብን ሐሳብ የያዘ ነው። ኢዮብ ክፉዎች እንዲሁ ብለዋል ብሎ ቢገምትም (21፥15 ይመ)፣ በቍ 9 ላይ የተመለከተውም ከኢዮብ በቀጥታ የተጠቀሰ አይደለም፤ ኤሊሁም፣ እግዚአብሔር ጻድቃንንና ክፉዎችን በአንድ ዐይን ይመለከታል (ከ9፥22፤ ከ21፥17፤ ከ24፥1-12 ጋር ያነጻጽሩ) ከሚለው ከኢዮብ ተደጋጋሚ ሐሳብ ይህንኑ ሳይጠቅስ አይቀርም። ይህም እግዚአብሔርን ማስደሰት የሚያስገኘው ጥቅም አይኖርም ወደሚለው መደምደሚያ ሐሳብ ያመራል።

34፥7 *ፌዝን እንደ ውሃ የሚጠጣት፤* ኤልፋዝ በ15፥16 ላይ ስለ ሰው የተናገረውን ይመ።

34፥10 *ክፋትን ማድረግ ከእግዚአብሔር ዘንድ… ይራቅ፤* ዘፍ 18፥25 እና ማብ ይመ። ኤሊሁን ያሳሰበው ኢዮብ እግዚአብሔርን የክፋት ምንጭ አድርጎ ማየቱ ነው፤ ይህም ኤሊሁን ያስመሰግነዋል። ኢዮብ ጭንቀት ውስጥ ሳለ ተስፋ ከመቍረጡ የተነሣ ሕይወቱን አደጋ ላይ በሚጥል ሁኔታ፣ እግዚአብሔርን እንደ ወንጀለኛ ቈጠረ (12፥4-6፤ 24፥1-12)። እርሱም ካለው ዕውቀትና ልምድ አኳያ (9፥24)፣ መደምደሚያ ነው ብሎ ማቅረብ የሚችለው ሐሳብ ይህንኑ ብቻ ነው።

*34፥11፤* 2ቆሮ 5፥10 ይመ።

*34፥13-15፤* ለሰው ሁሉ ሕይወትንና እስትንፋስን በመስጠት ጸጋውን ለሚያሳየው፣ ተንከባካቢ ለሆነው፣ ለእግዚአብሔር ክብር ኤሊሁ ከፍተኛ ቅናት አለው።

34፥15 *ወደ ዐፈር በተመለሰ፤* መክ 12፥7 እንዲሁም ዘፍ 3፥19 እና ማብ ይመ።

34፥16 *ስማ… አድምጥ፤* እነዚህ ግሶች በዕብራይስጡ በነጠላ ቍጥር መቀመጣቸው ሐሳቡ የተነገረው ለአንድ ሰው ያውም ለኢዮብ መሆኑን ያሳያሉ። ኤሊሁ የእግዚአብሔርን ፍትሕ በተመለከተ ኢዮብ ያለው አመለካከት እንዲስተካከል ይፈልጋል (ቍ 17 ይመ)፤ ስለዚህም ኤሊሁ እግዚአብሔር የማያዳላ የሁሉ ጌታ፣ በተለይም በከፍተኛ ሥልጣን ላይ ላሉት ጨቋኝ ሹሞች የእጃቸውን የሚሰጣቸው መሆኑን በአጽንዖት ይናገራል (ቍ 18-20)።

34፥18 *ክፉዎች፤* የዘዳ 13፥13 ማብ ይመ።

*34፥21-28፤* እግዚአብሔር ሁሉን ዐዋቂ ስለሆነ ክፉዎችን ሲቀጣ ከቶ አይሳሳትም፤ ሰዎችን መርምሮ ፍርድ ለመስጠት የጊዜ ቀጠሮ አያስፈልገውም (ቍ 23 ይመ፤ ከ24፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

*34፥21፤* ኤሊሁ በ31፥4 ላይ ያለውን የኢዮብን ንግግር እዚህ ላይ ይደግመዋል።

34፥29 *እርሱም ዝም ቢል ማን ሊወቅሰው ይችላል?* ኢዮብ ስለ እግዚአብሔር ዝምታ ላቀረበው ብሶት (ም 23) ኤሊሁ መልስ ይሰጣል፤ እግዚአብሔር፣ ትክክል የሆነውን ነገር በሰዎችና በመንግሥታት ዘንድ የቱን ያህል በመፈጸም ላይ እንደሚገኝ ይመለከታል (ቍ 29-30)።

ፊቱንስ ቢሰውር፣ ማን ሊያየው
ይችላል?
እርሱ ከሰውም፣ ከሕዝብም በላይ ነው፤
[30]ይህም የሆነው ዐመፀኛው ሕዝቡን
እንዳይገዛ፣
ወጥመድም በፊታቸው እንዳይዘረጋ ነው።
[31]“ሰው ለእግዚአብሔር እንዲህ ቢል፣ የተሻለ
ነበር፤
‘እኔ በደለኛ ነኝ፤ ከእንግዲህ ግን
አልበድልም፤
[32]ማየት ያልቻልሁትን አስተምረኝ፤
ኀጢአት ሠርቼ እንደ ሆነም፣ ደግሜ
አልሠራም።’
[33]ታዲያ አንተ ለመናዘዝ ፈቃደኛ ሳትሆን፣
እግዚአብሔር እንደ ወደድህ ይከፍልሃልን?
መወሰን ያለብህ አንተ ነህ እንጂ፣ እኔ
አይደለሁም፤
እንግዲህ የምታውቀውን ንገረኝ።
[34]“አስተዋዮች ይናገራሉ፤
የሚሰሙኝም ጠቢባን እንዲህ ይሉኛል፤
[35]‘ኢዮብ ያለ ዕውቀት ይናገራል፤
ቃሉም ማስተዋል ይጐድለዋል።’
[36]ምነው ኢዮብ እስከ መጨረሻ በተፈተነ
ኖሮ!
እንደ ክፉ ሰው መልሶአልና፤
[37]በኀጢአቱም ላይ ዐመፅን ጨምሮአል፤
በመካከላችን ሆኖ በንቀት
አጨብጭቦአል፤
በእግዚአብሔርም ላይ ብዙ ተናግሮአል።

## 35

ኤሊሁ ንግግሩን በመቀጠል እንዲህ አለ፤
[2]“ ‘በእግዚአብሔር ፊት ንጹሕ ነኝ’[a] ማለትህ፣
ትክክል ይመስልሃልን?
[3]ደግሞ ‘ያገኘሁት[b] ጥቅም ምንድን ነው?
ኀጢአት ባለመሥራቴስ ምን
አተረፍሁ?’ ብለህ ጠይቀኸዋል።
[4]“ለአንተና አብረውህ ላሉት ባልንጀሮችህ፣
መልስ መስጠት እፈልጋለሁ።
[5]ቀና ብለህ ወደ ሰማይ እይ፤
ከአንተ በላይ ከፍ ብለው ያሉትንም
ደመናት ተመልከት።
[6]ኀጢአትህስ ቢበዛ እርሱን ምን
ትጐዳዋለህ?
ኀጢአትህስ ቢበዛ ምን ያደርገዋል?
[7]ጻድቅ ብትሆንም ለእርሱ ምን
ትሰጠዋለህ?
ከእጅህስ ምን ይቀበላል?
[8]ክፋትህ የሚጐዳው እንዳንተ ያለውን ሰው
ብቻ ነው፤
ጽድቅህም የሚጠቅመው የሰውን ልጆች
ብቻ ነው።
[9]“ሰው ከጭቈና ብዛት የተነሣ ይጮኻል፤
ከኀያሉም ክንድ ሥር ለመውጣት
ለርዳታ ይጣራል።
[10]ነገር ግን እንዲህ የሚል የለም፤ ‘ፈጣሪዬ
እግዚአብሔር ወዴት ነው?
በሌሊት መዝሙርን የሚሰጥ፣
[11]ከምድር እንስሳት ይልቅ የሚያስተምረን፣
ከሰማይ ወፎችም ይልቅ ጠቢባን
የሚያደርገን፣ እርሱ የት አለ?’
[12]ከዐመፀኞች ትዕቢት የተነሣ፣
ሰዎች ሲጮኹ አይመልስላቸውም፤
[13]በእርግጥ እግዚአብሔር ከንቱ ጩኸታቸውን
አይሰማም፤
ሁሉን የሚችል አምላክ አያዳምጣቸውም።
[14]ጉዳይህን ፊቱ አቅርበህ፣
ብዙ ጠብቀኸው፣
ግን እንዳላየኸው ስትናገር፣
ታዲያ፣ አንተን እንዴት ይሰማህ!
[15]ደግሞም፣ ቍጣው ቅጣት
እንደማያስከትል፣
ኀጢአትንም[c] ከቍጥር እንደማያስገባ
ተናግረሃል።
[16]ስለዚህ ኢዮብ አፉን በከንቱ ይከፍታል፤
ዕውቀት አልባ ቃላትንም ያበዛል።

[a]2 ወይም፣ ጽድቄ ከእግዚአብሔር ጽድቅ ይበልጣል
[b]3 ወይም፣ ያገኘው
[c]15 ሲማኩስ፣ ቴዎዶቲዮንና ቩልጌት ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ ነገር ግን በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጒም አይታወቅም

34፥30 ቍ17፤ኢዮ 8፥13፤መዝ25፥15፤31፥4፤91፥3፤124፥7፤140፥5፤ምሳ29፥2-12
34፥31 መዝ51፥5፤ሉቃ15፥21፤ሮሜ7፥24፤1ዮሐ1፥8፡10
34፥32 ዘፀ33፥13፤ኢዮ33፥27፤35፥11፤38፥36፤መዝ15፥2፤25፥4፤27፥11፤51፥6፤86፥11፤139፥23-24፤143፥8፤ሉቃ19፥8
34፥33 2ነገ17፥13፤ኢዮ33፥23፤36፥10፡15፡18፡21፤41፥11፤42፥6፤ምሳ17፥23፤ዮና3፥8
34፥35 ኢዮ26፥3፤35፥16፤38፥2፤42፥3
34፥36 ኢዮ6፥29፤22፥15
34፥37 ኢዮ23፥2፤27፥23፤35፥16
35፥2 ኢዮ2፥9፤32፥2፤33፥32
35፥3 ኢዮ9፥29-31፤21፥15
35፥5 ዘፍ15፥5፤ዘዳ10፥14፤ኢዮ11፥7-9፤መዝ19፥1-4
35፥6 ኢዮ7፥20
35፥7 ኢዮ22፥2-3፤ሉቃ17፥10፤ሮሜ11፥35፤1ቆሮ4፥7
35፥8 ሕዝ18፥5-9፡24፤ዘካ7፥9-10
35፥9 ዘፀ2፥23፤ኢዮ5፥15፤12፥19፤20፥19
35፥10 ኢዮ4፥17፤8፥21፤መዝ42፥8፤77፥6፤119፥62፤149፥5፤ሐሥ16፥25
35፥11 ኢዮ12፥7፤21፥22፤ሉቃ12፥24
35፥12 1ሳሙ8፥18፤ኢዮ15፥25፤መዝ66፥18
35፥13 ዘዳ1፥45፤1ሳሙ8፥18፤ኢዮ15፥31፤ምሳ15፥8
35፥14 ኢዮ9፥11፤31፥35፤መዝ37፥6
35፥15 ኢዮ9፥24፤18፥5፤መዝ10፥11፤ሆሴ7፥2፤አሞ8፥7

*34፥31-33፤* ኤሊሁ በመጀመሪያ በተዘዋዋሪ መንገድ (ቍ 31-32) በኋላም በቀጥታ መንገድ (ቍ 33) ኢዮብን በመውቀስ ንስሓ እንዲገባ ይጋብዘዋል።

34፥35 *ኢዮብ ያለ ዕውቀት ይናገራል፤* በመጀመሪያው የእግዚአብሔር ንግግር ይህ ዋናው ሐሳብ ሲሆን (38፥2 ይመ)፣ በኢዮብ የመጨረሻው ንግግርም ዋና ሐሳብ ይህ ነው (42፥3 ይመ)።

*35፥1-16፤* ኤሊሁ ለኢዮብ የተናገረው ሦስተኛው ንግግር ነው (የ32፥1-37፥24 ማብ ይመ)።

35፥2 *ንጹሕ፤* ከዚህ ቃል ጋር ተመሳሳይ የሆነው የዕብራይስጥ ቃል በ13፥18 ላይ፣ “ይፈርድልኛል” ተብሎ ተተርጒሞአል። ኢዮብ በአንድ በኩል እግዚአብሔር በደል የሌለብኝ መሆኔን ያረጋግጥልኛል እያለ፣ ይህን ባለበት አፉ እኛ ጻድቃን ብንሆን ወይም ባንሆን እግዚአብሔር ግድ የለውም ማለቱ፣ በኤሊሁ ዘንድ ሲታይ ትክክልና አንድ አፍ ሆኖ አለመገኘት ነው (ቍ 3 ይመ)። ነገር ግን አንድ ሰው በተለያየ ወቅት የተለያየ ስሜት ሊገልጽ እንደሚችል መገንዘብ ተገቢ ነው። እግዚአብሔርን የናፈቀው መዝሙረኛ (42፥1-2)፣ እግዚአብሔር ለምን እንደ ረሳውና (መዝ 42፥9) ለምንስ እንደ ተወው (43፥2) ጠይቆአል።

35፥5 *ቀና ብለህ ወደ ሰማይ እይ፤* እግዚአብሔር ከሰው በላይ ከፍ ብሎ የሚገኝ ስለ ሆነ ሰው በእግዚአብሔር ባሕርይ ላይ ደግሞም ሆነ ክፉ ነገር ማምጣት እንደማይችል ኤሊሁ ያረጋግጣል (ቍ 6 ይመ)።

35፥9 *ሰው… ይጮኻል… ለርዳታ ይጣራል፤* እንደ ኢዮብ ያሉ ሰዎች ያለአበሳቸው ሥቃይ ደርሶባቸው በሚጸልዩበት ጊዜ የጥበብና የደስታ ምንጭ የሆነው (ቍ 10-11) ፈጣሪያቸው ቅንፈራጅና ርኅሩኅ እንደ ሆነ ማመን እንደሚያቅታቸው ኤሊሁ ይገልጻል። ይህ ዐይነቱ አለማስተዋል የእብሪት ምልክት ነው (ቍ 12 ይመ)፤ እንዲሁም ኢዮብ ስለ እግዚአብሔር ፍትሕና ዝምታ ያቀረበው ብሶት ትርጒም አልባ ንግግር ነው (ቍ 13-16 ይመ)።

35፥10-11 *መዝሙርን የሚሰጥ… የሚያስተምረን… ጠቢባን የሚያደርገን፤* እግዚአብሔር ሰውን በፍቅሩ ለመጥራት ራሱን ውሱን አድርጎ ለመቅረብ ፈለገ።

*35፥12፤* ሰዎች የሚጮኹት ከክፉዎች ትዕቢት የተነሣ ነውን? ሰዎች ትዕቢተኞች በመሆናቸው እግዚአብሔር አይሰማቸውም (ቍ 13 ይመ)፤ ኢዮብ ራሱ ክፉ ሰው ባይሆንም፣ በትዕቢቱ ግን ከእነርሱ ጋር ይመሳሰላል። ስለዚህ አግባብ ባለው መልክ ልመናውን ባለማቅረቡ እርሱም መልስ አላገኘም (ቍ 14 ይመ)።

*35፥16፤* እዚህ ላይ ኢዮብ በሦስተኛ መደብ ቢጠቀስም፣ ከኢዮብ ሌላ የተለየ ሰው አለ ማለት አይደለም (ቍ 1-16 ማብ ይመ)። *አልባ፤* 38፥2 እና ማብ ይመ። *ቃላትም ያበዛል፤* በእግዚአብሔር ላይ ስሞታ በማሰማት ማለት ነው (34፥37 ይመ)።

# 36

ኤሊሁ በመቀጠል እንዲህ አለ፤
[2]"በእግዚአብሔር ፈንታ ሆኜ የምለው አለኝ፤
ጥቂት ታገሠኝና እነግርሃለሁ::
[3]ዕውቀቴን ከሩቅ አመጣለሁ፤
ፈጣሪዬ ጻድቅ እንደ ሆነ እገልጻለሁ::
[4]ቃሌ ሐሰት እንዳልሆነ አረጋግጣለሁ፤
በዕውቀቱ ፍጹም የሆነ ሰው ከአንተ ጋር ነው::

[5]"እግዚአብሔር ኀያል ነው፤ ግን ማንንም አይንቅም፤
ኀያል፣ በዐላማውም ጽኑ ነው::
[6]ክፉዎችን በሕይወት አያኖርም፤
ለተቸገሩት ግን በቅን ይፈርዳል::
[7]ዐይኖቹን ከጻድቃን ላይ አያነሣም፤
ከነገሥታት ጋር በዙፋን ላይ ያስቀምጣቸዋል፤
ለዘላለምም ከፍ ከፍ ያደርጋቸዋል::
[8]ነገር ግን ሰዎች በሰንሰለት ቢታሰሩ፣
በመከራም ገመድ ቢጠፈሩ፣
[9]በእብሪት የፈጸሙትን በደል፣
ተግባራቸውን ይነግራቸዋል::
[10]ተግሣጽን እንዲሰሙ ያደርጋቸዋል፤
ከክፋታቸውም እንዲመለሱ ያዛቸዋል::
[11]ታዘው ቢያገለግሉት፣
ቀሪ ዘመናቸውን በተድላ፣
ዕድሜያቸውንም በርካታ ይፈጽማሉ::
[12]ባይሰሙ ግን፣
በሰይፍ[a] ይጠፋሉ፤
ያለ ዕውቀትም ይሞታሉ::

[13]"ልባቸው ከእግዚአብሔር የራቀ፣ ቍጣን ያስተናግዳሉ፤
በሰንሰለት ባሰራቸውም ጊዜ እንኳ ወደ እርሱ አይጮኹም::
[14]በቤተ ጣዖት ውስጥ ዝሙት በሚፈጽሙት መካከል፣
ገና በወጣትነታቸው ይቀጫሉ::
[15]ነገር ግን የሚሠቃዩትን ከሥቃያቸው ያድናቸዋል፤
በመከራቸውም ውስጥ ይናገራቸዋል::

[16]"አንተንም ከመከራ መንጋጋ፣
ጭንቀት ወደሌለበት ወደ ሰፊ ስፍራ፣
ምርጥ ምግብ ወደ ሞላበት ማእድ ያወጣሃል::
[17]አሁን ግን ለክፉዎች የሚገባው ፍርድ በላይህ ተጭኖአል፤
ፍርድና ብይን ይዘውሃል::
[18]ባለጠግነት እንዳያታልልህ፣
የእጅ መንሻ ብዛትም እንዳያስትህ ተጠንቀቅ::
[19]ባለጠግነትህም ሆነ ብርቱ ጥረትህ ሁሉ፣
ችግር ውስጥ እንዳትገባ ሊረዳህ ይችላልን?
[20]ሰዎች ከቤታቸው[b] የሚወሰዱበትን፣
ሌሊት አትመኝ::
[21]ከመከራ ይልቅ መርጠኸዋልና፣
ወደ ክፋት እንዳትመለስ ተጠንቀቅ::

[22]"እነሆ፤ እግዚአብሔር በኀይሉ ከፍ ከፍ ብሎአል፤
እንደ እርሱስ ያለ አስተማሪ ማን ነው?
[23]እርሱን መንገድ የሚመራው፣
ወይም 'ይህን አጥፍተሃል' የሚለው ማን ነው?
[24]ሰዎች በመዝሙር ያወደሱትን፣
የእርሱን ሥራ ማወደስ አትዘንጋ::

35፥16 ኢዮ34፥35፡37፤1ቆሮ4፥20፤ቲቶ1፥10፤ይሁ1፥10
36፥3 ኢዮ4፥17፤6፥28
36፥4 ኢዮ6፥28፤13፥6፤32፥17፤37፥5፡16፡23
36፥5 ዘኍ23፥19፤ኢዮ9፥4፤መዝ5፥2፤22፥24፤31፥22፤69፥33፤102፥17፤103፥10፤ሮሜ11፥29
36፥6 ኢዮ4፥10፤34፥26
36፥7 1ሳሙ2፥7-8፤ኢዮ4፥7፤11፥11፤መዝ11፥5፤33፥18፤34፥15፤113፥8፤ኢሳ22፥23፤ማቴ6፥18
36፥8 ቍ10፡15፡21፤2ሳሙ3፥34፤2ነገ23፥33፤መዝ107፥10፡14፤119፥67፡71
36፥9 ኢዮ15፥25
36፥10 ቍ8፤መሳ6፥8፤ኢዮ5፥17፤33፥16፤34፥33፤1ተሰ5፥22
36፥11 ዘፀ8፥22፤ዘሌ26፥33፤ዘዳ8፥1፤28፥1፤30፥15፤ኢዮ8፥7፤ኢሳ1፥19፤ሐጌ1፥12፤ዮሐ14፥21፤1ጢሞ4፥8
36፥12 ዘሌ26፥38፤ኢዮ4፥21፤15፥22፤ኤፌ4፥18
36፥13 ኢዮ4፥17፤5፥2፤15፥12፤አሞ4፥11፤ሮሜ2፥5
36፥14 ዘዳ23፥17፤ኢዮ15፥32
36፥15 ቍ8፥ኢዮ5፥15፤33፥16፤34፥33፤2ቆሮ12፥10
36፥16 ዘፍ17፥1፤2ሳሙ22፥20፤አዮ15፥11፤መዝ18፥19፤23፥5፤78፥19፤118፥5፤ሆሴ2፥14

36፥17 ኢዮ20፥29፤22፥11 36፥18 ዘፀ23፥8፤ኢዮ34፥33፤አሞ5፥12 36፥19 መዝ49፥6፤ኤር9፥23 36፥20 ኢዮ34፥20፡25 36፥21 ቍ8፤ኢዮ34፥33፤መዝ66፥18፤ዕብ11፥25 36፥22 ኢዮ5፥9፤9፥4፤21፥22፤ሮሜ11፥34 36፥23 ዘፍ18፥25፤ኢዮ27፥11፤34፥10፡13፤ሮሜ11፥33 36፥24 ዘፀ15፥1፤1ዜና16፥24፤መዝ35፥27፤92፥5፤111፥2፤138፥5፤145፥10፤ራእ15፥3

[a]12 ወይም፣ *ወንዙን ያቋርጣሉ*
[b]20 በዕብራይስጥ ከቍ18-20 ያለው ክፍል ትርጕሙ በትክክል አይታወቅም

*36፥1-37፥24፤* በአብዛኛው ለኢዮብ የተነገረ ሲሆን (የ37፥2 ማብ ይመ)፣ አራተኛውና የመጨረሻው የኤሊሁ ንግግር (36፥2፤ የ32፥1-37፥24 ማብ ይመ) ነው::

36፥4 *በዕውቀቱ ፍጹም የሆነ፤* እዚህ ላይ ኤሊሁ በዚህ ሐረግ የራሱን ማንነት ሲገልጽ በ37፥16 ላይ ደግሞ የእግዚአብሔርን ማንነት ለመግለጽ ተጠቅሞበታል፤ ይሁን እንጂ በዚህ ስፍራ ዕብራይስጡ፣ "ዕውቀት" የሚለው ቃል በ13፥16 ላይ ካለው ቃል ጋር አንድ አይደለም:: እዚህ ላይ ኤሊሁ የፈለገው ሐሳቡን በንግግር የመግለጽ ችሎታው ከፍተኛ መሆኑን ለማሳየት ሳይሆን አይቀርም፤ ይኸውም በንግግር ችሎታው ያለውን ፍጹምነት ለማሳየት ነው (የ32፥6፡10፡17 ማብ ይመ)::

*36፥5፤* የእግዚአብሔር ዕቅድ ተፈጻሚ እንደሚሆን ኀያል ሥልጣኑ ማረጋገጫ ነው::

*36፥6-9፤* እግዚአብሔር ጻድቃንን እንደሚሸልም፣ ኀጢአተኞችን ግን እንደሚቀጣ የሚገልጽ ነባር የሆነ ሐሳብ ነው (ይህም ኢዮብ ከሚለው ነገር ጋር የሚጻረር ነው):: ኢዮብ እግዚአብሔር እንደማይተወው የተናገረው ነገር፣ በኤሊሁ አእምሮ ውስጥ የነበረ ይመስላል (ቍ 7) (7፥17-19 ይመ)፤ በቍ 9 ላይ ደግሞ እግዚአብሔር በእርሱ ላይ ክስ እንደሚያቀርብበት ኢዮብ የተናገረውን ኤሊሁ ልብ ሳይል አልቀረም (31፥35-36 ይመ)::

36፥10 *ተግሣጽን እንዲሰሙ ያደርጋቸዋል፤* ኤሊሁ እግዚአብሔር የሰውን ልብ ለመሳብ ችግርን መሣሪያ አድርጎ እንደሚጠቀምበት ይገልጻል::

*36፥12፤* ወንዙን ይሻገራሉ ማለት ሲሆን፣ ይኸውም ወደ ወዲያኛው ዓለም ይሻገራሉ እንደማለት ነው (የ33፥18 ማብ ይመ)::

*36፥13-15፤* የሰው መንፈሳዊ ችግሩ መንሥኤ ልቡ ደንዳና መሆኑ፣ ለእግዚአብሔር እሺ ብሎ ያለመገዛቱ፣ በጭንቅ ላይ ሳለ ወደ እግዚአብሔር መጮኸ ያለመፈለጉ (መዝ 107 ይመ) ወይም በሥቃይ ውስጥ ሳለ የእግዚአብሔርን ድምፅ ለመስማት እሺ ባይ ሆኖ ባለመገኘቱ መሆኑን ኤሊሁ ያምናል::

36፥14 *በቤተ ጣዖት ውስጥ ዝሙት በሚፈጽሙት፤* የ1ነገ 14፥24 ማብ ይመ::

*36፥16-21፤* ኢዮብ ከክፋት ተመልሶ የእግዚአብሔርን ተግሣጽ አሜን ብሎ ይቀበል ዘንድ (ቍ 21 ይመ)፣ ኤሊሁ ያስጠነቅቀዋል:: ኤሊሁ በቍ 16 ላይ ኢዮብ አሁንም እንኳ ያለው ሰው መሆኑን ይገልጻል::

36፥16 *አንተንም... ያወጣሃል፤* እግዚአብሔር በምሕረቱና በርኅራኄው ሕዝቡን ወደ ራሱ ይመልሳል (ሆሴ 2፥14 ይመ)::

36፥21 *ወደ ክፋት እንዳትመለስ ተጠንቀቅ፤* ኤሊሁ ስለ ኢዮብ ያለው ግምት እግዚአብሔር ለኢዮብ ካለው ግምት ጋር ይቃረናል (1፥8፤ 2፥3 ይመ)::

*36፥22-23፤* በም 38-41 ላይ የተመለከተው የእግዚአብሔር ሐሳብ ምን እንደሚመስል ቀደም አድርጎ ይናገራል::

36፥24 *ሰዎች በመዝሙር ያወደሱትን... ሥራ፤* ዘፀ 15፥1፤ መሳ 5፥1 ይመ::

[25]ሰው ሁሉ አይቶታል፤
ሰዎችም በትኵረት ተመልክተውታል።
[26]እነሆ፤ እግዚአብሔር ከአእምሯችን በላይ
ታላቅ ነው!
የዘመኑም ቍጥር ከመታወቅ ያልፋል።
[27]"የውሃን ነጠብጣብ ወደ ላይ ያተናል፤
መልሰም በዝናብ መልክ በጅረቶች ላይ
ያወርዳል፤
[28]ደመናት ጠል ያንጠባጥባሉ፤
ዶፍም በሰው ላይ ይወርዳል።
[29]ደመናትን እንዴት እንደሚዘረጋ፣
ከድንኳኑም እንዴት እንደሚያንጐደጕድ
ሊረዳ የሚችል ማን ነው?
[30]መብረቁን በዙሪያው እንዴት
እንደሚበትን ተመልከት፤
የባሕሩንም ወለል ይሸፍናል።
[31]እርሱ ሕዝብን የሚያስተዳድረው፣[ዘ]
ምግብንም አትረፍርፎ የሚሰጣቸው
በዚህ መንገድ ነው።
[32]እጆቹን በመብረቅ ይሞላቸዋል፤
ዒላማውንም እንዲመታ ያዝዘዋል።
[33]ነጐድጓዱ ውሽንፍር እንደሚከተለው
ያመለክታል፤
ከብቶችም እንኳ መምጣቱን ይጠቍማሉ።

# 37

ልቤ በዚህ በኀይል ይመታል፤
ከስፍራውም ዘለል ዘለል ይላል።
[2]ስሙ! የድምፁን ጩኸት ስሙ፤
ከአፉ የሚወጣውን ጕርምርምታ
አድምጡ።
[3]መብረቁን ከሰማይ ሁሉ በታች
ያባርቃል፤
ወደ ምድርም ዳርቻ ይልካል።
[4]ከዚያም በኋላ የድምፁ ጩኸት ይመጣል፤
በድምፁም ግርማ ያንጐደጕዳል፤
ድምፁ በተሰማ ጊዜ፣
መብረቁን የሚከለክል የለም።
[5]የእግዚአብሔር ድምፅ በሚያስደንቅ ሁኔታ
ያንጐደጕዳል፤
እኛ የማናስተውለውንም ታላቅ ነገር
ያደርጋል።
[6]በረዶውን፣ 'በምድር ላይ ውደቅ'
ውሽንፍሩንም 'ዶፍህን አውርደው' ይላል።
[7]እርሱ የፈጠራቸው ሰዎች ሁሉ ሥራውን
ያውቁ ዘንድ፣
እያንዳንዱ ሰው እንዳይሠራ ይገታዋል።[+]
[8]እንስሳት ይጠለላሉ፤
በየዋሻቸውም ይቈያሉ።
[9]ዐውሎ ነፋስ ከማደሪያው፣
ብርድም ከብርቱ ነፋስ ይወጣል።
[10]የእግዚአብሔር እስትንፋስ በረዶ ያስገኛል፤
ሰፋፊ ውሆች ግግር በረዶ ይሆናሉ።
[11]ደመናትን ርጥበት ያሸክማቸዋል፤
መብረቁንም በውስጣቸው ይበትናል።
[12]ያዘዘውን ለመፈጸም፣
እርሱ በሚሰጠው መመሪያ፣
በመላው የምድር ገጽ ላይ ይሽከረከራሉ።
[13]ሰዎችን ለመቅጣት ደመና ያመጣል፤
ወይም በዚሁ ምድሩን አጠጥቶ[ፀ] ፍቅሩን
ይገልጻል።
[14]"ኢዮብ ሆይ፤ ይህን ስማ፤
ቆም ብለህ የእግዚአብሔርን ድንቅ ሥራ
ዐስብ።
[15]እግዚአብሔር ደመናትን እንዴት
እንደሚቈጣጠር፣
መብረቁንም እንዴት እንደሚያበርቅ
ታውቃለህን?
[16]ደመናት ሚዛን ጠብቀው እንዴት
እንደሚንሳፈፉ፣
በዕውቀቱ ፍጹም የሆነውን፣ የእርሱን
ድንቅ ሥራ ታውቃለህን?
[17]ምድር በደቡብ ነፋስ ጸጥ ባለች ጊዜ፣
ከሙቀት የተነሣ በልብስህ ውስጥ
የምትዝለፈለፍ ሆይ፤
[18]ከቀለጠ ናስ እንደ ተሠራ መስተዋት
የጠነከረውን ሰማይ ሲዘረጋ፣
አብረኸው መዘርጋት ትችል ነበርን?

36፥25 ሮሜ1፥20
36፥26 ዘፍ21፥33፤ ኢዮ5፥9፤ 10፥5፤ 1ቆሮ13፥12፤ዕብ1፥12
36፥27 2ሳሙ1፥21 ፤ኢዮ26፥8፤28፥26፤ 38፥28፤ኢሳ55፥10
36፥28 ኢዮ5፥10፤ 22፥11፤28፥26፤መዝ 65፥10፤72፥6፤ኢል 2፥23፤ማቴ5፥45
36፥29 ኢዮ9፥6፤ 37፥16፤መዝ18፥7-15 ፤19፥4:5፤29፥3፤104፥ 2፤ምሳ8፥28፤ኢሳ40፥ 22፤ኤር10፥13
36፥30 ዘፀ19፥16፤ ኢዮ37፥11:15፤መዝ 18፥12:14፤68፥22፤ 97፥4፤ኢሳ51፥10፤ ኤር10፥13፤ዕን3፥11
36፥31 ዘዳ28፥23-24፤1ነገ17፥1፤ኢዮ 37፥13፤መዝ104፥14-15:27-28፤145፥15፤ ኢሳ30፥23፤አሞ4፥7-8፤ሐሥ14፥17
36፥32 ኢዮ28፥24፤ 37፥12:15፤መዝ18፥ 14፤29፥7-9
36፥33 ኢዮ28፥26፤ 37፥5፤40፥9
37፥1 መዝ38፥10፤ ኢሳ15፥5፤ኤር4፥19 ፤ዕን3፥16
37፥2 ቍ5፤ኢዮ32፥ 10፤መዝ18፥13፤29፥ 3-9
37፥3 2ሳሙ22፥ 13፤ኢዮ36፥32፤መዝ 18፥14፤ማቴ24፥27፤ ሉቃ17፥24
37፥4 ዘፀ20፥19፤ 1ሳሙ2፥10
37፥5 1ሳሙ2፥10፤ ኢዮ5፥9፤11፥7-9፤ 36፥4:33፤ዮሐ12፥29
37፥6 ዘፍ7፥4፤ዘዳ 28፥12፤ኢዮ5፥10፤ 28፥26፤38፥22
37፥7 መዝ104፥19-23፤109፥27፤111፥2
37፥8 ኢዮ28፥26፤ 38፥40፤መዝ104፥22
37፥9 መዝ50፥3፤ 147፥17
37፥10 ኢዮ38፥29-30፤መዝ147፥17
37፥11 ኢዮ26፥8፤28፥26፤36፥30 37፥12 ቍ3፤መዝ147፥16፤ 148፥8 37፥13 ዘፍ7፥4፤ዘፀ9፥22-23፤1ሳሙ12፥17፤1ነገ18፥45፤ ኢዮ5፥10፤36፥31፤38፥27 37፥14 ኢዮ5፥9፤32፥10 37፥15 ኢዮ 36፥30:32 37፥16 ኢዮ5፥9፤36፥4:29 37፥17 ሐሥ27፥13
37፥18 ዘፍ1፥1፤ዘዳ28፥23፤ኢዮ22፥14

[ዘ]30 ወይም፣ *የሚያስተዳድረው*
[+]7 ወይም፣ *ሰዎችን ሁሉ በኀይሉ ያስፈራቸዋል ማለትም ነው*
[ፀ]13 ወይም፣ *ፍቅሩንም ለመግለጽ ደመናን ያመጣል*

36፥26 *ከአእምሯችን በላይ፤* 37፥5 ይመ። የእግዚአብሔር መንገድና ሐሳብ ከሰው መንገድና አስተሳሰብ እጅግ የላቀ መሆኑን የም 38-41 ላይ ያለው ክፍል መሠረታዊ ትምህርት ነው።

36፥30 *ይሸፍናል፤* በቁሙ፣ "ያለብሰዋል" ማለት ሲሆን፣ የባሕሩ ውስጠኛ ክፍል በብርሃን መሙላቱን ያሳያል።

36፥31 *የሚያስተዳድረው፤* ጌታ በቍ 27-30 ላይ በተመለከተው ክፍል ጠል ሕዝቦችን እንደሚመግብ ያመለክታል።

36፥32 *እጆቹን፤* እግዚአብሔር በኀያል ሥልጣኑ የፈቀደውን ሁሉ እንደሚያከናውን ያመለክታል (ኢሳ 55፥10-11 ይመ)።

*37፥1-13፤* በምድር የሚታየውን የእግዚአብሔር ታላቅነት ለመግለጽ ኤሊሁ በ36፥27 ላይ የጀመረውን ንግግር በዚህ ክፍልም ቀጥሎ እናያለን፤ ከተገለጸውም ታላቅ ክብር የተነሣ ልቡ ቀልጦአል (ቍ 1 ይመ)። ክፍሉ በአየር ውስጥ የሚፈጸሙትን ውስብስብ ነገሮች ይገልጻል፤ ይኸውም ውሃ ተንኖ ወደ ሰማይ ከወጣ በኋላ ወደ ዝናብ እንደሚለወጥ (36፥27 ይመ)፣ ደመና እርጥብ አየር እንደሚሸከም (36፥28፤ 37፥11 ይመ)፣ እንዲሁም የዐውሎ ነፋስ ባሕርይ ዐዟሉ እንደሚገኝ ነው (ቍ 12 ይመ)። የእነዚህ ሁሉ ኀይላት መሠረት የእግዚአብሔር ትእዛዝ ሲሆን፣ መልካምም ሆነ ክፉ (ቍ 13) የእግዚአብሔር ፈቃድ በሰው ዘር ሁሉ ላይ ይፈጸማል።

37፥2 *ስሙ፤* የዕብራይስጡ ግስ እንደዚሁ የብዙ ቍጥር ሲሆን፣ ከኢዮብ ሌላ ሌሎችንም (ሦስቱንም ጓደኞች ጭምር) የሚመለከት ነው (የ36፥1-37፥4 ማብ ይመ)። *ከአፉ የሚወጣውን ጕርምርምታ፤* ነጐድጓድ ማለት ነው (ቍ 4 ይመ)።

37፥5 *እኛ የማናስተውለውንም፤* የ36፥26 ማብ ይመ።

37፥10 *የእግዚአብሔር እስትንፋስ፤* ለቀዝቃዛ አየር የተሰጠ ዘይቤያዊ ንግግር ነው።

*37፥14-18፤* እግዚአብሔር በፍጥረታት ላይ የቱን ያህል ኀያል እንደ ሆነ ያስተውል ዘንድ ለኢዮብ የቀረበ ማሳሰቢያ ነው። ይህ ዐይነቱ የጥያቄ ስልት በመለኮት ንግግርም ላይ ይታያል (ም 38-41)።

37፥16 *በዕውቀቱ ፍጹም የሆነውን፤* የ36፥4 ማብ ይመ።

37፥18 *ሰማይ ሲዘረጋ፤* 26፥7 ይመ። *ናስ... የጠነከረውን፤* በዘዳ 28፥23 ላይ የናስ ሰማይ የሚለው ስዕላዊ ገለጻ ዝናብ አልባ ሙቀትን የሚያመለክት ነው (በዚያ የሚገኘውን ማብ ይመ)።

[19]"ከጨለማችን የተነሣ እኛ ጕዳያችንን
መግለጽ አንችልም፤
ለእርሱ የምንለውን ንገረን።
[20]እኔ መናገር እንደ ፈለግሁ ሊነገረው
ይገባልን?
ይዋጥ ዘንድ የሚጠይቅ ሰው አለን?
[21]እንግዲህ ነፋስ ሰማያትን ካጠራ በኋላ፣
እጅግ የምታብረቀርቀውን ፀሓይ፣
ሊመለከት የሚችል የለም።
[22]እንደ ወርቅ በሚያበራ ክብር ከሰሜን
ይወጣል፤
እግዚአብሔር በሚያስፈራ ግርማ ይመጣል።
[23]ሁሉን የሚችል አምላክ ከአእምሯችን
በላይ ነው፤ በኀይልና በፍርድ ታላቅ
ነው፣
ጽድቁም ብዙ ነው፤ ማንንም
አይጨቍንም።
[24]ስለዚህ፣ ሰዎች ይፈሩታል፤
በልባቸው[+] አስተዋዮች እንደ ሆኑ
የሚያስቡትን አይመለከትም?"

## እግዚአብሔር ተናገረ

**38** እግዚአብሔርም በዐውሎ ነፋስ ውስጥ ሆኖ ለኢዮብ መለሰለት፤
እንዲህም አለው፤

[2]"ዕውቀት በጐደለው ቃል፣
ዕቅዴን የሚያጨልም ይህ ማን ነው?
[3]እስቲ እንደ ወንድ ወገብህን ታጠቅ፤
እኔ ልጠይቅህ፣
አንተም መልስልኝ።
[4]"ምድርን በመሠረትሁ ጊዜ አንተ የት
ነበርህ?
በእርግጥ የምታስተውል ከሆንህ፣
ንገረኝ።

37፥19 ኢዮ9፥31 13፥18፤ሮሜ8፥26
37፥21 መሳ5፥31፤ሐሥ22፥11፤ 26፥13
37፥22 ዘፀ24፥17፤ መዝ19፥5
37፥23 ኢዮ4፥17፤ 5፥9፤8፥3፤36፥4፤መዝ 44፥1፤ኢሳ63፥9፤ኤር 25፥5፤ሰቆ3፥33፤ሕዝ 18፥23፡32፤ሮሜ11፥ 33፤1ጢሞ6፥16
37፥24 ዘፍ22፥12፤ ኢዮ5፥13፤28፥28፤መ ክ12፥13፤ሚክ6፥8፤ማ ቴ10፥28፤ኤፌ5፥15
38፥1 ዘፀ14፥21፤ 1ሳሙ2፥10፤ኢዮ11፥ 5፤40፥6፤ኢሳ21፥ 1፤ሕዝ1፥4
38፥2 1ነገ22፥5፤ ኢዮ34፥35፤ኢሳ40፥ 13፤ማር10፥38፤ 1ጢሞ1፥7
38፥3 ኢዮ40፥7፤ 42፥4፤ማር11፥29
38፥4 ቍ5፡18፤ዘፍ 1፥1፤1ሳሙ2፥8፤ኢዮ 34፥13፤ምሳ30፥4
38፥5 ቍ4፤መዝ 102፥25፤ምሳ8፥29፤ ኢሳ40፥12፤48፥13፤ ኤር31፥37፥39፤ዘካ 1፥16፤4፥9-10
38፥6 ኢዮ26፥7፤ ምሳ8፥25
38፥7 ዘፍ1፥16፤ዘዳ 16፥15፤1ነገ22፥19፤ መዝ19፥1-4፤148፥2-3
38፥8 ቍ11፤ ዘፍ1፥9-10፤መዝ33፥ 7፤ምሳ8፥29፤ኤር5፥22
38፥9 ዘፍ1፥2
38፥10 ነህ3፥3፤ኢዮ 7፥12፤26፥10፤28፥25 1፤መዝ33፥7፤104፥9፤

[5]ካወቅህ፣ መጠኗን ለይቶ ማን ወሰነ?
በላይዋስ መለኪያ ገመድ የዘረጋ ማን ነው?
[6]መሠረቶቿ ምን ላይ ተተከሉ?
የማእዘን ድንጋይዋንስ ማን አቆመ?
[7]ይህም የሆነው የንጋት ከዋክብት
በዘመሩበት ጊዜ፣
መላእክትም[*] እልል ባሉበት ጊዜ ነበር።
[8]"ባሕር ከማሕፀን በወጣ ጊዜ፣
በር የዘጋበት ማን ነው?
[9]ደመናውን ልብሱ፣
ጨለማንም መጠቅለያው አደረግሁለት፣
[10]ድንበር ወሰንሁለት፤
መዝጊያና መወርወሪያውን አበጀሁለት።
[11]'እስከዚህ ድረስ ትመጣለህ፤ ማለፍ ግን
አትችልም፤
የዕቡይ ማዕበልህም ገደብ ይህ ነው'
አልሁት።
[12]"ከተወለድህ ጀምሮ ንጋትን አዘህ
ታውቃለህን?
ወይስ ወጋገን ስፍራውን እንዲይዝ
አድርገሃል?
[13]በዚህም የምድርን ዳርቻ ይዞ፣
ክፉዎችን ከላይዋ እንዲያራግፍ
አድርገሃልን?
[14]ምድር ከማኅተም በታች እንዳለ የሸክላ
ጭቃ ቅርጿ ይወጣል፤
ቅርጿ እንደ ልብስ ቅርጽ ጐልቶ
ይታያል።

ኢሳ40፥12 38፥11 ቍ8፤መዝ65፥7፤89፥9፤104፥6-9 38፥12 መዝ57፥8፤74፥16፤አሞ5፥8 38፥13 ኢዮ8፥22፤መዝ104፥35 38፥14 ዘፀ28፥11

+24 ወይም፣ *በልባቸው አስተዋዮች ወደ ሆኑ*
*7 ወይም፣ *የእግዚአብሔር ልጆች*

37፥19 *ጕዳያችንን መግለጽ አንችልም፤* ኢዮብ የመከላከያ ሐሳብ ለማቅረብ ድፍረት በማግኘቱ እግዚአብሔር ያደምጠው ዘንድ ይጠይቃል (31፥35 ይመ)። በዚህም ጕዳይ ኤሊሁ ሊያሳፍረው ይፈልጋል፤ ይሁን እንጂ እርሱም ከእግዚአብሔር ሞገስ አኳያ ሲታይ ከበደል ንጹሕ ባለመሆኑ በኢዮብ ላይ ሊሰነዝር ያሰበውን፣ "እኛ" በማለት አለሳልሶ ያቀርባል።

37፥22 *ከሰሜን... ይወጣል፤* የመዝ 48፥2 ማብ ይመ። *እግዚአብሔር... ይመጣል፤* እግዚአብሔር በማዕበል ራሱን ለሚገልጥበት ቀን ኤሊሁ ኢዮብን ያዘጋጀል (ም 38-41)።

37፥24 *ይፈሩታል፤* 28፥28፤ ዘፍ 20፥11 እና ማብ ይመ)።

*38፥1-42፥6፤* እግዚአብሔርም ለኢዮብ ተገልጦአል፤ ሁለት ጊዜም አነጋግሮታል (38፥1-40፥2፤ 40፥6-41፥34)፤ ኢዮብም ለእያንዳንዱ ንግግር ምላሽ ሰጥቶአል (40፥3-5፤ 42፥1-6)።

38፥1 *እግዚአብሔር፤* ያህዌ የሚለው ስም እስራኤላውያን አምላክን የሚጠሩበት የቃል ኪዳን ስም ነው። *በዐውሎ ነፋስ፤* 40፥6 ይመ። ኤሊሁ የእግዚአብሔርን መገለጥ "የወርቅ ጌጥ" ወይም "የሚያስደንቅ ግርማ" አድርጎ ቈጥሮታል (37፥22)። ኢዮብ የእግዚአብሔርን ድምፅ የሰማው ከዐውሎ ነፋስ እንደ ሆነም ኤሊሁ ገምቶአል (የ37፥22 ማብ ይመ)። ኢዮብም "ሁሉን የሚችል አምላክ መልስ ሰጠኝ" (31፥35) አለ፤ የእግዚአብሔርንም መልስ ተቀበለ።

*38፥2፤* 35፥16 ይመ። በ42፥3 ላይ ኢዮብ የጌታን ቃል ይደግመዋል ኢዮብ በእግዚአብሔር ላይ መመረርና መቈጣት ከአእምሮው ውስንነት የመነጨ መሆኑን ያመለክታል።

*38፥3፤* በ40፥7 ላይ ተደግሞአል (42፥4 ይመ)። እግዚአብሔር ሲመልስ የተጠቀመባቸው መልስ አዘል ጥያቄዎች እያንዳንዳቸው የኢዮብን አለማወቅ የሚያሳዩ ናቸው። ስለ ኢዮብ ሥቃይ ወይም ኢዮብ ስለ መለኮታዊ ፍትሕ የነበረውን ጥያቄ አስመልክቶ እግዚአብሔር ምንም የተናገረው ነገር የለም። ኢዮብም በደለኛ ወይም ንጹሕ ሰው ስለ መሆኑ የተቀበለው ማስረጃ የለም። መሠረታዊው ነገር ግን እግዚአብሔር አሳሳፈረውም፤ አልኰነነውምም የዚህም እንድምታ ኢዮብ ነጻ መውጣቱን፤ በኋላም ነጻነቱ በቀጥታ መረጋገጡን ያሰያል (42፥7 ይመ)። መለኮታዊው ንግግር ለኢዮብ ጥያቄ ቀጥተኛ መልስ ሳይሰጥ፣ ኢዮብ በእግዚአብሔር ቸርነት በሙሉ ልቡ እንዲያምን አደረገው።

*38፥4-38፤* ሕያዋን ያልሆኑ ፍጥረታት እንኳ የእግዚአብሔርን ሉዓላዊነትና ኀይል ይመሰክራሉ (ምድር ቍ 4-7፡18፤ ባሕር ቍ 8-11፡16፤ ፀሓይ ቍ 12-15፤ የሙታን ዓለም ቍ 17፤ ብርሃንና ጨለማ ቍ 19-20፤ የአየር ጠባይ ቍ 22-30፡34-38፤ የከዋክብት ስብስብ ቍ 31-33)፤ የ38፥39-39፥30 ማብ ይመ።

*38፥4-5፤* አጉር የተናገረውን ተመሳሳይ ጥያቄና ምጸት ከምሳ 30፥4 ይመ።

*38፥7፤* መዝ 148፥2-3 ይመ። እንዲሁም የመዝ 65፥13 ማብ ይመ። ምድር በምትፈጠርበት ጊዜ የሰማይ መላእክት ፈጣሪን ለማመስገን በዚያው ነበሩ፤ ኢዮብ ግን በዚያ ስፍራ አልነበረም (ቍ 4-5 ይመ)፤ ስለዚህ ኢዮብ እግዚአብሔር ለዓለምና ለሰው ልጆች ያለውን ዕቅድ ሁሉ ይቅርና ጥቃቅን ነገር እንኳ እንደሚያውቅ አድርጎ ራሱን መገመት የለበትም።

*38፥10-11፤* መዝ 33፥7፤ ኤር 5፥22 ይመ።

38፥11 *አልሁት፤* እግዚአብሔር አብ እንደ እግዚአብሔር ወልድ (ሉቃ 8፥24-25 ይመ) ባሕርን በቃሉ ያዛል።

*38፥12-13፤* የብርሃኑ መውጣት ክፉዎች በቅጽበት በጎፍረት እንዲዋጡ ያደርጋቸዋል።

38፥14 ከማኅተም በታች እንዳለ የሸክላ ጭቃ፤ ክብ የሆነ ማኅተም (የዘፍ 38፥18 ማብ ይመ) ወይም የማኅተም መርገጫ ማለት ሊሆን ይችላል።

[15]ክፉዎች ብርሃናቸውን ተከልክለዋል፤
ከፍ ያለው ክንዳቸውም ተሰብሮአል።

[16]"ወደ ባሕር ምንጭ ወርደህ ታውቃለህን?
ወይስ ወደ ጥልቀቱ ገብተህ በመሠረቱ
ላይ ተመላልሰሃልን?
[17]የሞት ደጆች ተገልጠውልሃልን?
የሞትንስ ጥላ በሮች አይተሃልን?
[18]የምድርን ስፋት ታውቃለህን?
ይህን ሁሉ ዐውቀህ ከሆነ፣ ንገረኝ።

[19]"ወደ ብርሃን መኖሪያ የሚያደርሰው
መንገድ የትኛው ነው?
የጨለማ መኖሪያስ ወዴት ነው?
[20]ወደ ማደሪያቸው ልትወስዳቸው
ትችላለህን?
የመኖሪያቸውን መንገድ ታውቃለህ?
[21]ያን ጊዜ ተወልደሃል! ዕድሜህ ትልቅ
ነውና፣
አንተስ በእርግጥ ሳታውቅ አትቀርም!

[22]"ወደ በረዶው መጋዘን ገብተሃልን?
የዐመዳዩንስ ማከማቻ አይተሃልን?
[23]ይኸውም ለመከራ ጊዜ፣
ለጦርነትና ለውጊያ ቀን ያስቀመጥሁት
ነው።
[24]መብረቅ ወደሚሰራጭበት ቦታ
የሚያደርሰው መንገድ፣
የምሥራቅም ነፋስ በምድር ላይ
ወደሚበተንበት ስፍራ የሚወስደው
የትኛው ነው?
[25]ለዝናብ መውረጃን፣
ለመብረቅም መንገድን ያበጀ ማን ነው?
[26]በዚህም ማንም የማይኖርበትን ምድር፣
ሰውም የሌለበትን ምድረ በዳ የሚያጠጣ፣
[27]ባድማውንና በረሓውን መሬት
የሚያጠግብ፣
ሣርም እንዲበቅልበት የሚያደርግ ማን
ነው?
[28]ዝናብ አባት አለውን?
የጤዛን ጠብታ ማን ወለደው?
[29]በረዶ ከማን ማሕፀን ይወጣል?
የሰማዩንስ ዐመዳይ ማን ይወልዳል?
[30]ውሆች እንደ ድንጋይ ይጠነክራሉ፤
የጥልቁ ገጽ እንደ በረዶ ይጋገራል።

[31]"ፕልያዲስ የተባሉትን ውብ ከዋክብት
ልትለጕም፣
ወይም የኦርዮንን ማሰሪያ ልትፈታ
ትችላለህን?
[32]ማዛሮት የተባለውን የከዋክብት ክምችት
በወቅቱ[a] ልታወጣ፣
ወይም ድብ የተባለውን ኮከብና ልጆቹን
ልትመራ ትችላለህ?
[33]የሰማያትን ሥርዐት ታውቃለህ?
ይህንስ በምድር ላይ እንዲሠለጥን
ማድረግ ትችላለህ?

[34]"ድምፅህን ወደ ደመናት አንሥተህ፣
ራስህን በጐርፍ ማጥለቅለቅ ትችላለህን?
[35]መብረቆችን መስደድ ትችላለህ?
እነርሱስ፣ 'እነሆ፤ እዚህ አለን' ይሉሃል?
[36]ለልብ[b] ጥበብን፣
ለአእምሮም ማስተዋልን የሰጠ ማን ነው?
[37]ትቢያ ሲጠጥር፣
ጓሎችም እርስ በርስ ሲጣበቁ፣
[38]ደመናትን ለመቍጠር ጥበብ ያለው
ማን ነው?
የሰማያትንስ የውሃ ገንቦ ዘንበል ማድረግ
ማን ይችላል?

[39]"ለአንበሳዪቱ አድነህ ግዳይ ታመጣለህን?
የተራቡ የአንበሳ ግልገሎችንስ
ታጠግባለህን?
[40]እነርሱ በዋሻ ውስጥ ያደባሉ፤
በደን ውስጥም ይጋደማሉ።
[41]ልጆቿ ወደ እግዚአብሔር ሲጮኹ፣
ምግብ አጥተው ሲንከራተቱ፣
ለቍራ መብልን የሚሰጥ ማን ነው?

# 39

"የበረሃ ፍየል የምትወልድበትን ጊዜ
ታውቃለህን?
ዋልያ ስታምጥስ ተከታትለህ
አይተሃል?
[2]የእርግዝናቸው ወራት ምን ያህል እንደ
ሆነ ትቈጥራለህን?
የሚወልዱበትንስ ጊዜ ታውቃለህን?
[3]ተንበርክከው ይወልዳሉ፤
ከምጣቸውም ጣር ይገላገላሉ።

38፥15 ዘፍ17፥14፤ ዘጸ28፥29፤ኢዮ4፥10፤ ኢዮ15፥22፤18፥5፤ 31፥22
38፥16 ዘፍ1፥7፤ ኢዮ9፥8
38፥17 ኢዮ7፥9፤ 33፥22፤ማቴ16፥18፤ ራእ1፥18
38፥18 ቍ4፤ኢዮ 28፥24፤ኢሳ40፥12
38፥19 ዘፍ1፥4፤ ኢዮ28፥3፤መዝ139፥ 11-12
38፥20 ኢዮ24፥13
38፥21 ኢዮ15፥7
38፥22 ዘጸ28፥12፤ ኢዮ37፥6፤መዝ105፥ 32፤147፥17
38፥23 ዘፀ9፥26፤ ኢሱ10፥11፤መዝ27፥ 5፤ኢሳ28፥17፤30፥30 ፤ሕዝ13፥11፡13፤ ራእ16፥21
38፥24 ኢዮ27፥21፤ 28፥24፤ኤር10፥13፤5 1፥16
38፥25 ኢዮ28፥26
38፥26 ኢዮ36፥27፤ መዝ84፥6፤107፥35፤ ኢሳ41፥18
38፥27 ኢዮ28፥26፤ 37፥13፤መዝ104፥14
38፥28 2ሳሙ1፥ 21፤ኢዮ5፥10
38፥29 መዝ147፥ 16-17
38፥30 ኢዮ37፥10
38፥31 ኢዮ9፥9፤ አሞ5፥8
38፥32 ዘፍ1፥16፤ 2ነገ23፥5፤ኢሳ13፥10 ፤40፥26፥45፥12፤ ኤር19፥13
38፥33 ዘፍ1፥16፤ መዝ148፥6፤ኤር31፥36
38፥34 ኢዮ5፥10፤ 22፥11
38፥35 ኢዮ36፥32
38፥36 ኢዮ9፥4፤ 12፥13፤34፥32፤ያዕ1፥5
38፥37 ኢሱ3፥16፤ ኢዮ22፥11
38፥38 ዘሌ26፥19፤ 1ነገ18፥45
38፥39 ዘፍ49፥9
38፥40 ዘፍ49፥9፤ ኢዮ37፥8
38፥41 ዘፍ1፥30፤ 8፥7፤መዝ147፥9፤ ማቴ6፥26፤ሉቃ12፥24 39፥1 ዘፍ49፥21፤ዘዳ14፥5 39፥2 ዘፍ31፥7-9

[a]32 ወይም *በወቅቱ የሚወጣ የንጋት ኮከብ*
[b]36 በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጕም በትክክል አይታወቅም

38፥15 *ብርሃናቸውን፤* ሌሊት፣ ክፉዎች የሚነቁበት ጊዜ ነው (ዮሐ 3፥19 ይመ፤ ለስዕላዊ ገለጻው ከሉቃ 11፥35 ጋር ያነጻጽሩ)። *ከፍ ያለው ክንዳቸውም ተሰብሮአል፤* 22፥9 እና ማብ ይመ።

38፥16 *ባሕር ምንጭ፤* ዘፍ 7፥11፤ 8፥2 ይመ።

38፥17 *የሞት ደጆች፤* የ17፥16 ማብ እንዲሁም የ26፥5-6 ይመ።

38፥22-23 *በረዶው... ለጦርነትና... ቀን፤* ኢሱ 10፥11፤ ኢሳ 28፥2 እና ማብ ይመ።

38፥24 *የምሥራቅም ነፋስ፤* የ15፥2 ማብ ይመ።

38፥31-32 *ፕልያዲስ... ኦርዮን... ድብ፤* የ9፥9 ማብ ይመ።

38፥36 *ለልብ... ለአእምሮም፤* የመጀምሪያውን ቃል፣ "የቈላ ወፍ" ሁለተኛውን ደግሞ፣ "አውራ ዶሮ" ብሎ መተርጐም ይቻላል፤ ሰዎች እነዚህን የአዕዋፍ ባሕርይ በመመልከት የአየሩን ሁኔታ አስቀድሞ ማወቅ ይችሉ ነበር፤ ነገሩ እንደዚያ ከሆነ ለሚቀጥለውና የመጀመሪያ ለሆነው ዐቢይ መለኮታዊ ንግግር ክፍል መሸጋገሪያ ነው።

*38፥39-39፥30፤* ሕያዋን ፍጡራን የእግዚአብሔርን ሉዓላዊነት፣ ኀይልና የፍቅር ጥበቃ ይመሰክራሉ፤ ለምሳሌ:- አንበሳ (38፥39-40)፤ ቍራ (38፥41)፤ የሚዳ ፍየሎች (39፥1-4)፤ የሚዳ አህያ (39፥5-8)፤ ጎሽ (39፥9-12)፤ ሰጎን (39፥13-18)፤ ፈረስ (39፥19-25)፤ ጭልፊት (39፥26)፤ ንስር (39፥27-30)፤ የ38፥4-38 ማብ ይመ።

38፥41 *ለቍራ መብልን የሚሰጥ፤* በዚህ ስፍራ ቍራ የወከለው እግዚአብሔር ለአዕዋፍ ሁሉ እንደሚጠነቀቅና የሚበሉትንም እንደሚሰጣቸው የሚያሳይ ነው (ለምሳሌ:- ሉቃ 12፥24 ከማቴ 6፥26 ጋር ያነጻጽሩ)።

39፥1 *ጊዜ ታውቃለህን?* ኢዮብ ሊመልስ የማይችለውን ጥያቄ እግዚአብሔር ያቀርብለታል፤ በዚህም መልኩ ከእግዚአብሔር ጋር ለመከራከር ያለው ምኞት የቱን ያህል ሞኝነት እንደ ሆነ ያሳየዋል።

4ግልገሎቻቸውም ይጠነክራሉ፤ በሜዳም
ያድጋሉ፤
ተለይተው ይሄዳሉ፤ ወደ እነርሱም
አይመለሱም።

5"ለሜዳ አህያ ነጻነት የሰጠው ማን ነው?
እስራቱንስ ማን ፈታለት?
6ምድረ በዳውን መኖሪያው፣
የጨውንም ምድር ማደሪያው አድርጌ
ሰጠሁት።
7በከተማ ውካታ ይሥቃል፤
የነጂውንም ጩኸት አይሰማም።
8በየተራራው ይሰማራል፤
ሐመልማሉንም ሁሉ ለማግኘት ይወጣል።

9"ጐሽ ያገለግልህ ዘንድ ይታዘዛልን?
በበረትህስ አጠገብ ያድራልን?
10እንዲያርስልህ ልትጠምደው ትችላለህ?
ወይስ እየተከተለህ ዕርሻህን
ይጐለጕልልሃልን?
11ጕልበቱ ብርቱ ስለ ሆነ
ትተማመንበታለህ?
ከባዱን ሥራህንስ ለእርሱ ትተዋለህ?
12እህልህን እንዲሰበስብልህ፣
በዐውድማህም ላይ እንዲያከማችልህ
ታምነዋለህን?

13"ሰጎን ክንፎቿን በደስታ ታራግባለች፤
ነገር ግን እንደ ሽመላ ላባዎች ሊሆኑ
አይችሉም።
14ዕንቍላሏን መሬት ላይ ትጥላለች፤
እንዲሞቅም በአሸዋ ውስጥ ትተወዋለች።
15እግር እንደሚሰብረው፤
የዱር አውሬም እንደሚረግጠው
አታስብም።
16የእርሷ እንዳልሆኑ ሁሉ በልጆቿ
ትጨክናለች፤
ድካሟም በከንቱ ቢቀር ደንታ የላትም፤
17እግዚአብሔር ጥበብ ነሥቶአታልና፤
ማስተዋልንም አልሰጣትም።
18ለመሸምጠጥም ክንፎቿን ስትዘረጋ፣
በፈረስና በጋላቢው ትሥቃለች።

19"ለፈረስ ጕልበትን ትሰጠዋለህን?
ዐንገቱንስ ጋማ ታለብሰዋለህን?
20እንደ አንበጣ የምታስዘልለው አንተ
ነህን?
የማንኰራፋቱም ግርማ አስፈሪ ነው።
21በጕልበቱ እየተመካ በብርቱ
ይጐደፍራል፤
ጦርነት ሊገጥም ይወጣል።
22ያለ አንዳች ሥጋት፣ በፍርሀት ላይ
ይሥቃል፤
ሰይፍ ቢመዘዝበትም ወደ ኋላ አይልም።
23ከሚብረቀረቀው ጦርና አንካሴ ጋር፣
የፍላጻው ኰረጆ ጐኑ ላይ ይንኳኳል።
24በወኔ መሬቱን እየጐደፈረ ወደ ፊት
ይሸመጥጣል፤
የመለከት ድምፅ ሲሰማ ያቅበጠብጠዋል።
25መለከቱ ሲያንባርቅ፣ 'እሰይ' ይላል፤
የአዛዦችን ጩኸትና የሰራዊቱን
ውካታ፣
ጦርነትንም ከሩቅ ያሸታል።

26"ጭልፊት የሚበረው፣
ክንፎቹንም ወደ ደቡብ የሚዘረጋው፣
በአንተ ጥበብ ነውን?
27ንስር ወደ ላይ የሚመጥቀው፣
ጎጆውንም በከፍታ ላይ የሚሠራው፣
በአንተ ትእዛዝ ነውን?
28በገደል ላይ ይኖራል፤ በዚያም ያድራል፤
ምሽጉም የቋጥኝ ጫፍ ነው።
29እዚያ ሆኖ የሚነጥቀውን ይቃኛል፤
ዐይኑም ከሩቅ አጥርቶ ያያል።
30ጫጩቶቹ ደም ይጠጣሉ፤
እርሱም በድን ካለበት አይታጣም።"

40 እግዚአብሔርም ኢዮብን እንዲህ
አለው፤
2"ሁሉን ከሚችል አምላክ ጋር ተከራክሮ
የሚረታው አለን?
እግዚአብሔርን የሚወቅስ እርሱ መልስ
ይስጥ!"

3ኢዮብም *ለእግዚአብሔር* እንዲህ ሲል መለሰ፤
4"እኔ ከንቱ ሰው፣ ምን እመልስልሃለሁ?
እጄን በአፌ ላይ እጭናለሁ።
5አንድ ጊዜ ተናገርሁ፤ የምመልሰው የለኝም፤
ሁለተኛም ተናገርሁ፤ ከእንግዲህ አንዳች
አልጨምርም"

39፥5 ዘፍ16፥12
39፥6 ኢዮ24፥5፤ 30፥4:7፤መዝ107፥34፤ኤር2፥24፤14፥6፤ 17፥6
39፥7 ኢዮ3፥18፤ 5፥22
39፥8 ኢሳ32፥20
39፥9 ዘፍ42፥27፤ ዘፀ21፥6፤ዘኍ23፥32
39፥10 ኢዮ41፥13፤ መዝ32፥9
39፥11 ቍ19፤ኢዮ 40፥16፤41፥12:22፤ መዝ147፥10
39፥13 ዘካ5፥9
39፥15 2ነገ14፥9
39፥16 ቍ17፤ ሰቆ4፥3
39፥17 ቍ16፤ኢዮ 21፥22
39፥18 ኢዮ5፥22
39፥19 ቍ11
39፥20 ኢዮ41፥25፤ ኤር8፥16፤ኢል2፥4-5፤ራእ9፥7
39፥21 ቍ11፤ ኤር8፥6
39፥22 ኢዮ5፥22
39፥23 ኢሳ5፥28፤ ኤር5፥16፤ናሆ3፥3
39፥24 ዘኍ10፥9፤ ኤር4፥5:19፤ሕዝ7፥14፤አሞ3፥6
39፥25 ኢሱ6፥5፤ ኤር8፥6፤አሞ1፥14፤ 2፥2
39፥26 ኤር8፥7
39፥27 ኤር49፥16፤ አብ1፥4፤ዕን2፥9
39፥28 ኤር49፥16፤ አብ1፥3
39፥29 ኢዮ9፥26
39፥30 ማቴ24፥28፤ሉቃ17፥37
40፥1 ኢዮ5፥8፤ 10፥2
40፥2 ኢዮ9፥3:15፤ 11፥8፤13፥3፤33፥13፤ ሮሜ9፥20
40፥4 መሳ18፥19፤ 29፥9፤42፥6
40፥5 ኢዮ9፥3:15

39፥5 *ለሜዳ አህያ፤* 24፥5 እንዲሁም በዘፍ 16፥12 ማብ ይመ ላይ ስለ እስማኤል የተጻፈውን ይመልከቱ።

*39፥9-12፤* የሜዳ አህያ ከቤት አህያ (ለማዳ አህያ) ጋር (ቍ 7) እንደ ተነጻጸረ ሁሉ ጎሽ ከበሬ ጋር ተነጻጽሮአል።

39፥11 *ብርቱ ስለ ሆነ፤* በብሉይ ኪዳን ጎሽ የጥንካሬ ምሳሌ ነው (ዘኍ 23፥22፤ 24፥8፤ ዘዳ 33፥17፤ መዝ 29፥6 ይመ)፤ እንደዚሁም ጎሽ ከዝሆንና ከአውራሪስ ቀጥሎ በትልቅነትና በኀይለኛነት የታወቀ የምድር እንስሳ ነበር።

*39፥13-18፤* በዚህ ክፍል እግዚአብሔር ኢዮብን የጠየቀው ጥያቄ ስለ ሌላ ከተደረገው ንግግር ሁሉ ለየት ያለ ነው፤ ይህ የሆነው ሰጎን አስደናቂ አእዋፍ በመሆኑ ሊሆን ይችላል?

39፥13 *እንደ ሽመላ ላባዎች፤* የሽመላ ላባዎች እጅግ አስደናቂዎች ናቸው (ዘካ 5፥9 ይመ)።

39፥18 *በፈረስና በጋላቢው፤* ወደሚቀጥለው አንቀጽ መሸጋገሪያ ነው።

*39፥19-25፤* በተደረገው ንግግር ውስጥ የቤት እንስሳ የሆነው ፈረስ ብቻ ነው፤ ይህ እውነታ ይሆናል ተብሎ የታሰበ ባይሆንም እንኳ፣ የጌታን ዐላማ ያሳካል፤ ከዚህም ላይ በተለይ የተመለከተው የጦር ፈረስ ነውና።

39፥20 *እንደ አንበጣ፤* ፈረስና አንበጣ በኤር 51፥27፤ እና በራእ 9፥7 ላይ ተነጻጽረዋል፤ ከኢል 2፥4 ጋር ያነጻጽሩ።

39፥26 *ጭልፊት፤* ጭልፊት በመካከለኛው ምሥራቅ የሚኖር አዕዋፍ አይደለም፤ ነገር ግን ክረምት ሲገባ በአገሩ ደቡባዊ ክፍል ወቅቱን ለማሳለፍ ጕዞ ሲያደርግ፣ ለተወሰነ ጊዜ በዚያ ቈይታ ያደርጋል።

39፥27 *ንስር፤* ምናልባት ጥምብ አንሣ አሞራ ሊሆን ይችላል (ቍ 30 ይመ)።

*40፥1-2፤* የመጀመሪያው መለኮታዊ ንግግር ማጠቃለያ ነው። ምላሽ ይሰጠው ዘንድ እግዚአብሔር ኢዮብን በድጋሚ ይጠይቀዋል።

*40፥3-5፤* እንደ "ንጉሥ" (31፥37) ሳይሆን በድንዛዜ፣ የምሬት ቃል ሳያሰማ ነገሩን የዳምጣል።

40፥4 *እኔ ከንቱ ሰው፤* የዕብራይስጡ ቃል፣ "ጥቂት" ወይም "አሳስፈላጊ" ማለትም ነው።

40፥5 *አንድ ጊዜ... ሁለተኛም፤* የ5፥19 ማብ ይመ።

[6]እግዚአብሔርም በዐውሎ ነፋስ ውስጥ
ሆኖ፣ ለኢዮብ እንዲህ ሲል ተናገረ፤
[7]“እንግዲህ እንደ ወንድ ወገብህን ታጠቅ፤
እኔ እጠይቅሃለሁ፤
አንተም መልስልኝ::
[8]“ፍርዴን ታቃልላለህን?
ወይስ አንተ ጻድቅ ለመሆን እኔን
ትኰንናለህ?
[9]እንደ እግዚአብሔር ክንድ ያለ ክንድ
አለህን?
ድምፅህስ እንደ እርሱ ድምፅ
ሊያንጐደጒድ ይችላልን?
[10]እንግዲያስ ክብርንና ልዕልናን ተጐናጸፍ፣
ግርማ ሞገስንም ተላበስ፤
[11]ቍጣህን አፍስስ፤
ትዕቢተኛውን ሁሉ ተመልክተህ
አዋርደው፤
[12]ትዕቢተኛውን ሰው ሁሉ ተመልክተህ ዝቅ
አድርገው፤
ክፉዎችንም በቆሙበት ስፍራ
አድቅቃቸው::
[13]ሁሉንም በአንድ ላይ ከዐፈር
ደባልቃቸው፤
ፊታቸውንም በመቃብር ውስጥ ሸፍን::
[14]እኔም ቀኝ እጅህ እንደምታድንህ፣
በዚያን ጊዜ አረጋግጬ እቀበላለሁ::
[15]“አንተን እንደ ፈጠርሁ፣ የፈጠርሁትን፣
‘ብሂሞት’[ገ] ጒማሬን ተመልከት፤
እንደ በሬ ሣር ይበላል፤
[16]ብርታቱ ወገቡ ውስጥ፣
ኀይሉም በሆዱ ጡንቻ ላይ ነው::
[17]ጅራቱ[ለ] እንደ ጥድ ዛፍ ይወዛወዛል፤
የወርቹ ጅማት የተጐነጐነ ነው::

40፥6 ዘፀ14፥21፤ ኢዮ38፥1
40፥7 ኢዮ38፥3
40፥8 ኢዮ2፥3፤ 15፥25፤27፥2፤34፥17 ፤ሮሜ3፥3
40፥9 ዘፀ20፥19፤ 2ዜና32፥8፤ኢዮ36፥ 33፤መዝ98፥1፤ኢሳ 6፥8፤ሕዝ10፥5
40፥10 መዝ29፥1-2፤45፥3፤93፥1፤96፥6፤ 104፥1፤145፥5
40፥11 ኢዮ20፥28፤ መዝ7፥11፤18፥27፤ ኢሳ2፥11፤5፥25፤9፥ 12፡19፤10፥5፤13፥3 ፡5፤23፥9፤24፥10፤25፥ 12፤26፥5፤30፥27፤32 ፥19፤42፥25፤51፥20፤ ኤር7፥20፤ናሆ1፥6፤ ሶፎ1፥18
40፥12 1ሳሙ2፥7፤ መዝ10፥4፤52፥5፤60፥ 12፤ኢሳ22፥5፤25፥11፤ 28፥3፤63፥2-3፡6፤ኤር 48፥29፤49፥16፤ዳን 5፥20፤ሚክ5፥8፤7፥10 ፤ሶፎ2፥10፤ዘካ10፥5፤ ሚል4፥3፤1ጴጥ5፥5
40፥13 ዘኍ16፥31-34፤ኢዮ4፥9
40፥14 ዘፀ15፥6፡ 12፤መዝ18፥35፤20፥ 6፤48፥10፤60፥5፤108 ፥6፤ኢሳ41፥10፤63፥5
40፥15 ኢዮ9፥9፤ ኢሳ11፥7፤65፥25
40፥16 ኢዮ39፥11፤ 41፥9
40፥17 ኢዮ41፥15
40፥18 ኢዮ41፥12፤ ኢሳ11፥4፤49፥2
40፥19 ዘፍ3፥24፤ ኢዮ4፥17፤9፥9፤41፥ 33፤መዝ40፥5፤139፥ 14፤ኢሳ27፥1

[18]ዐጥንቱ እንደ ናስ ቱቦ፣
እጅና እግሮቹም እንደ ብረት ዘንግ
ናቸው::
[19]እርሱ የእግዚአብሔር ሥራ አውራ ነው፤
በሰይፍ ሊቀርበውም የሚችል ፈጣሪው
ብቻ ነው::
[20]ኰረብቶች ምግቡን ያበቅሉለታል፤
አውሬዎችም ሁሉ በዙሪያው ይፈነጫሉ::
[21]በውሃ ላይ በሚያድጉ ዕፀዋት ጥላ ሥር
ይተኛል፤
በረግረግ ስፍራ ደንገል መካከል
ይደበቃል::
[22]በውሃ ላይ የሚያድጉ ዕፀዋት በጥላቸው
ይጋርዱታል፤
የወንዝ አኻያ ዛፎች ይሸፍኑታል::
[23]ወንዙ በኀይል ቢጐርፍም፣ አይደነግጥም፤
ዮርዳኖስ እስከ አፉ ቢሞላም፣ እርሱ
ተረጋግቶ ይቀመጣል::
[24]ዐይኑን ሸፍነህ ልትይዘው፣
አጥምደህም አፍንጫውን ልትበሳ
ትችላለህ?

# 41

“ሌዋታንን[ሀ] በመንጠቆ ልታወጣው፣
ወይም ምላሱን በገመድ
ልታስረው ትችላለህን?
[2]መሰንጊያ በአፍንጫው ልታስገባ፣
ወይም ጒንጩን በሜንጦ ልትበሳ
ትችላለህን?

40፥20 ኢዮ5፥23፤መዝ104፥14፡26 40፥21 ዘፍ41፥2፤ኢዮ 8፥11፤መዝ68፥30፤ኢሳ35፥7 40፥22 መዝ1፥3፤ኢሳ44፥4 40፥23 ኢሱ3፥1፤ኢሳ8፥7፤11፥15 40፥24 2ነገ19፥28፤ኢዮ41፥2፡7፡26፤ ኢሳ37፥29 41፥1 ኢዮ3፥8፤አሞ4፥2 41፥2 ኢዮ40፥24፤ሕዝ19፥4

[ገ]15 ጒማሬ ወይም ዝሆን
[ለ]17 ምናልባት ግንዱ ማለት ሊሆን ይችላል
[ሀ]1 ምናልባት ዐዞ ሊሆን ይችላል

*40፥6፤* 38፥1 እና ማብ ይመ::

*40፥7፤* ከ38፥3 ላይ ተደግሞአል (በዚያ ያለውን ማብ ይመ)::

*40፥8-14፤* ለሁለተኛው መለኮታዊ ንግግር መግቢያ ሲሆን በ41፥34 ላይ ይደመደማል:: እንደ መጀምሪያው የንግግር ክፍል ሳይሆን፣ እግዚአብሔር በዚህ ስፍራ እርሱ ጻድቅ እንደ ሆነ በአንጻሩ ደግሞ ኢዮብ ራሱን ጻድቅ አድርጎ መመልከት ከንቱ እንደ ሆነ ይናገራል:: ኢዮብ በም 21 እና በም 24 ላይ እግዚአብሔር የክፉ ሰዎችን እኵይ ምግባር በተመለከተ ግድ እንደ ሌለው ገልጾ ነበር፤ ነገር ግን በዚህ ስፍራ ኢዮብ ጽድቅን ለማስፈን ችሎታ ባይኖረውም እንኳ እግዚአብሔር ጽድቅን ለማስፈን ውሳኔውም ሆነ ችሎታው እንዳለው ይናገራል:: ስለዚህ የዚህ ተግሣጽ እንድምታ ኢዮብ ራሱን ማጽደቁንና ይህን ሁሉ መተው እንዳለበት የሚያስተምር ነው (ቍ 14)፣ እነዚህ ሁሉ ነገሮች ከእግዚአብሔር ብርቱ እጅ በታች ናቸው (ቍ 9 ይመ)::

40፥8 *ጻድቅ ለመሆን እኔን ትኰንናለህ?* ኢዮብ በ19፥6 ላይ እግዚአብሔር በድሎኛል ብሎአል::

40፥10 *ክብርንና ልዕልናን ተጐናጸፍ፤* የዕብራይስጡ በመዝ104፥1 ላይ “ክብርንና ግርማን ለበስህ” ብሎ እግዚአብሔርን ይገልጸዋል:: ኢዮብ ችሎታ ካለው ራሱን አምላክ እንዲያደርግ እግዚአብሔር ጥያቄውን ያቀርባል::

*40፥11-12፤* እነዚህን ነገሮች ጌታ ራሱ እንደሚፈጽም በኢሳ 13፥11 ላይ ተገልጾአል::

40፥13 *ከዐፈር፤* የ7፥21 ማብ ይመ::

40፥14 *ቀኝ እጅህ እንደምታድንህ፤* ከመዝ 49፥7-9 ጋር ያነጻጽሩ (ማብ ይመ)::

*40፥15-24፤* ከሁለቱ ቅኔዎች የመጀመሪያው ሲሆን (ም 41 ሁለተኛውን ግጥም ይዞአል)፣ እያንዳንዱ ክፍል ግዙፍ የዱር እንስሳን የሚገልጽ ነው፣ የተቋረጠውንም ስለ እንስሳት የሚያወራውን ክፍል የጀምራል ም 39::

40፥15 *ብሂሞት፤* ቃሉ የዕብራይስጥ ሲሆን፣ ትርጒሙም “አውሬ” ማለት ነው፤ በየብስ የሚኖር ግዙፍ እንስሳንም ያመለክታል:: እርሱን ለመግለጽ በቍ 16-24 ላይ ያሉት ቃላት ፍጹም ቅኔያዊና ግነትን የተሞሉ ናቸው:: *የፈጠርሁትን፤* ከእግዚአብሔር ፍጥረት መካከል አንዷ ተረት አይደለም::

40፥18 *ብረት፤* የ19፥24 ማብ ይመ::

40፥19 *የእግዚአብሔር ሥራ አውራ ነው፤* የዕብራይስጡ ቃል፣ “የሥራው መጀመሪያ” የሚል ትርጒም አለው፤ ይህም በስዕላዊ ገለጻ የጥበብን መጀመር የሚያሳይ ነው (ምሳ 8፥12:22) ይመ:: እዚህ ላይ የሚገኘው ገላጭ ሐረግ የግዙፍ እንስሳት ምሳሌ የሆነው፣ “ብሂሞት” በልዑል እግዚአብሔር ቍጥጥር ሥር መሆኑን ያሳያል::

40፥21-23 *በረግረግ ስፍራ ደንገል... አኻያ ዛፎች... ዮርዳኖስ፤* ከገሊላ ባሕር በስተ ሰሜን የሚገኘው “ሁሌ” የተባለውን አካባቢ የሚገልጽ ሳይሆን አይቀርም::

*40፥24፤* ብሂሞትና በ41፥1 ላይ የተጠቀሰው ሌዋታን በተመሳሳይ ዘዴ መያዛቸውን ያመለክታል::

*41፥1-34፤* ከሁለቱ ቅኔዎች የመጨረሻው ሲሆን፣ የእግዚአብሔርም የመጨረሻ ንግግር ነው (የ40፥15-24 ማብ ይመ)::

41፥1 *ሌዋታንን፤* ብሉይ ኪዳን ይህን ቃል የሚጠቀምበት በተምሳሌታዊና በቀጥታ ትርጒም ነው:: ዘይቤያዊ አነጋገሩን በተመለከተ የ3፥8 ማብ ይመ፤ ሌዋታን እጅግ ግዙፍ የባሕር እንስሳ ነው (መዝ 104፥26 ይመ)፤ እዚህ ላይ ግን ዐዞን ሳያመለክት አይቀርም:: (አማራጭ ትርጒሙን ይመ):: በዚህ ምዕራፍ ውስጥ የተገለጸው ሌዋታን በም 40 ላይ ከተጠቀሰው ብሂሞት ይልቅ እጅግ በጣም አስፈሪ እንስሳ ነው::

[3]እርሱ እንድትምረው ይለማመጥሃል?
በለስላሳ ቃላትስ ይናገርሃል?
[4]ለዘላለም ባሪያ ታደርገው ዘንድ፣
ከአንተ ጋር ይዋዋላልን?
[5]እንደ ወፍ አልምደኸው ከእርሱ ጋር
ልትጫወት ትችላለህ?
ወይስ ለሴት አገልጋዮችህ መጫወቻነት
ታስረዋለህን?
[6]ነጋዴዎችስ በእርሱ ላይ ይከራከራሉን?
ለቸርቻሪዎችስ ያከፋፍሉታል?
[7]ቈዳው ላይ አንካሴ ልትሰካ፣
ጭንቅላቱንም በዓሣ መውጊያ ጦር
ልትበሳ ትችላለህን?
[8]እርሱን እስቲ ንካው፣
ግብግቡን ታስታውሳለህ፤ ከቶም
አያላምድህም::
[9]እርሱን በቍጥጥር ሥር አውላለሁ ማለት
ዘበት ነው፤
በዐይን ማየት እንኳ ብርክ ያስይዛል::
[10]ሊቀሰቅሰው የሚደፍር የለም፤
ማን ፊቱ ሊቆም ይችላል?
[11]ነክቶት በሰላም የሚሄድ ማን ነው?
ከሰማይ በታች ማንም የለም::

[12]"ስለ ብርታቱና ስለ አካላቱ ውበት፣
ስለ እጅና እግሩ ከመናገር
አልቈጠብም::
[13]የደረበውን ልብስ ማን ሊያወልቅ ይችላል?
ማንስ ሊለጒመው ወደ መንጋጋው
ይቀርባል?
[14]አስፈሪ ጥርሶቹ የተገጠገጡበትን፣
የአፉን ደጅ ማን ደፍሮ ይከፍታል?
[15]ጀርባው፣ አንድ ላይ የተጣበቁ፣
የጋሻ ረድፎች አሉት፤
[16]እጅግ የተቀራረቡ ስለ ሆኑ፣
ነፋስ በመካከላቸው አያልፍም፤
[17]እርስ በርስ የተገጣጠሙ ናቸው፤
አንዱ ከአንዱ ጋር ተጣብቆአልና ማንም
ሊለያያቸው አይችልም::
[18]እንጥሽታው የብርሃን ብልጭታ ያወጣል፤
ዐይኖቹም እንደ ማለዳ ጮራ ናቸው::
[19]ከአፉ ፍም ይወጣል፤
የእሳት ትንታግ ይረጫል::
[20]በሸምበቆ ማገዶ ላይ ከተጣደ ድስት
እንደሚወጣ እንፋሎት፣
ከአፍንጫው ጢስ ይትጐለጐላል::
[21]እስትንፋሱ ከሰል ያቀጣጥላል፤
የእሳትም ነበልባል ከአፉ ይወጣል::
[22]ብርታት በዐንገቱ ውስጥ አለ፤
አሸባሪነትም በፊቱ እመር እመር
ይላል::
[23]የሥጋው ንብርብር እርስ በርስ የተጣበቀ፣
በላዩ የጸናና ከቦታው የማይናጋ ነው::
[24]ደረቱ እንደ ዐለት የጠጠረ፣
እንደ ወፍጮ ድንጋይም የጠነከረ ነው::
[25]እርሱ በተነሣ ጊዜ፣ ኀያላን ይርዳሉ፤
በሚንቀሳቀስበትም ጊዜ ወደ ኋላ
ያፈገፍጋሉ::
[26]ጦር፣ ፍላጻ ወይም አንካሴ፣
ሰይፍም ቢያገኘው አንዳች አይጐዳውም::
[27]እርሱ ብረትን እንደ አገዳ፣
ናስንም እንደ ነቀዘ ዕንጨት ይቈጥራል::
[28]ቀስት አያባርረውም፤
የወንጭፍ ድንጋይም ለእርሱ እንደ
ገለባ ነው::
[29]ቈመጥ በእርሱ ፊት እንደ ገለባ ነው፤
ጦር ሲሰበቅ ይሥቃል::
[30]የሆዱ ሥር እንደ ሸካራ ገል ነው፤
እንደ መውቂያ መሣሪያም በጭቃ ላይ
ምልክት ጥሎ ያልፋል::
[31]እንደሚፈላ ምንቸት ጥልቁን
ያናውጠዋል፤
ባሕሩንም እንደ ሽቶ ብልቃጥ
ያደርገዋል::
[32]ያለፈበትን መንገድ ብሩህ ያደርጋል፤
ቀላዩንም ሽበት ያወጣ ያስመስለዋል::
[33]ያለ ፍርሀት የተፈጠረ፣
እንደ እርሱ ያለ በምድር ላይ የለም::
[34]ከፍ ያሉትን ሁሉ በንቀት ይመለከታል፤
በትዕቢተኞችም ሁሉ ላይ ንጉሥ ነው::"

## ኢዮብ

# 42

ኢዮብም እንዲህ ሲል *ለእግዚአብሔር* መለሰ፤

[2]"አንተ ሁሉን ማድረግ እንደምትችል፣
ዕቅድህም ከቶ እንደማይሰናከል
ዐወቅሁ::
[3]አንተ፣ 'ያለ ዕውቀት ዕቅዴን
የሚያደበዝዝ ይህ ማን ነው' አልኸኝ፤
በእርግጥ ያልገባኝን ነገር፣
የማላውቀውንና ላስተውለው
የማልችለውን ጒዳይ ተናገርሁ::
[4]" 'ስማኝ፣ ልናገር
እኔ እጠይቃለሁ፤
አንተ ትመልስልኛለህ' አልኸኝ::

41፥4 1ነገ20፥31
41፥7 ኢዮ40፥24
41፥8 ኢዮ3፥8
41፥9 ኢዮ40፥16
41፥10 2ዜና20፥6፤ኢዮ3፥8፤ኢሳ46፥5፤ኤር50፥44፤ራእ6፥17
41፥11 ኢሱ3፥11፤ኢዮ10፥4፤34፥33፤ሐሥ4፥24፤ሮሜ11፥35፤1ቆሮ10፥26
41፥12 ኢዮ39፥11፤40፥18
41፥13 ኢዮ30፥11፤39፥10
41፥14 መዝ22፥13
41፥15 ኢዮ40፥17
41፥18 ኢዮ3፥9
41፥19 ዳን10፥6
41፥20 መዝ18፥8
41፥21 ኢዮ4፥9፤መዝ18፥8፤ኢሳ10፥17፤11፥4፤30፥27፤33፥14፤40፥7፤66፥14-16፤ኤር4፥4
41፥22 ኢዮ39፥11
41፥24 ማቴ18፥6
41፥25 ኢዮ3፥8፤39፥20
41፥26 ኢሱ8፥18፤ኢዮ40፥24
41፥27 ቍ29
41፥28 መዝ91፥5
41፥29 ቍ27፤ኢዮ5፥22
41፥30 ኢሳ28፥27፤41፥15፤አሞ1፥3
41፥31 1ሳሙ2፥14፤ሕዝ32፥2
41፥33 ኢዮ40፥19
41፥34 ኢዮ28፥8፤መዝ18፥27፤101፥5፤131፥1፤ምሳ6፥17፤21፥4፤30፥13
42፥2 ዘፍ18፥14፤2ዜና20፥6፤ኢዮ16፥19፤ማቴ19፥26፤ሐሥ4፥28፤ኤፌ1፥11
42፥3 ኢዮ5፥9፤34፥35
42፥4 ኢዮ38፥3

ቍ 11 አንዳንድ ትርጒሞች፣ "በዕዳ የሚጠይቀኝ ማን ነው? ከሰማይ በታች ያለው ሁሉ ንብረቴ ነው" ይላሉ::

*41፥10፤* ሌዋታን ብርቱ እንስሳ ነው፤ እግዚአብሔር ግን እጅግ ኀያል አምላክ ነው::

*41፥11፤* በቀጥታ አይሁን እንጂ ሐዋርያው ጳውሎስ በሮሜ 11፥35 ላይ ጠቅሶታል ተብሎ ይታሰባል::

41፥14-15 *አስፈሪ ጥርሶቹ... የአፉን ደጅ... ጀርባው... የጋሻ ረድፎች አሉት፤* የዐዞ ባሕርይ ነው::

*41፥18-21፤* እጅግ ተምሳሌታዊ ነው፤ የተጋነነ ቅኔያዊ አቀራረብ ነው::

41፥27 *ብረትን፤* የ19፥24 ማብ ይመ::

41፥30 *እንደ ሸካራ ገል፤* የተሰባበረ የሸክላ ዕቃ ነው::

41፥34 በትዕቢተኞችም ሁሉ ላይ ንጉሥ ነው፤ እነዚህን ፍጥረታት ሊያዋርድ የሚችለው እግዚአብሔር ብቻ ነው:: እግዚአብሔር እንዲሞክረው ቢነግረውም እንኳ ኢዮብ ይህን ያደርጋል ተብሎ አይጠበቅም (40፥11-12 ይመ)::

*42፥1-6፤* ለሁለተኛው የእግዚአብሔር ንግግር ኢዮብ የተናገረው የመጨረሻ ንግግር ነው::

*42፥2፤* ኢዮብ በመጨረሻ እግዚአብሔር ሆን የእግዚአብሔር ዐላማ እጅግ ምጡቅ እንደ ሆነ ተመልክቶአል::

*42፥3፤* ኢዮብ በ38፥2 ላይ ያለውን የእግዚአብሔርን ቃል ይጠቅሳል::

42፥4 *አልኸኝ፤* ኢዮብ በ38፥3 እና በ40፥7 ላይ ያለውን የእግዚአብሔርን ቃል ይጠቅሳል::

[5]ጆሮዬ ስለ አንተ ሰምታ ነበር፤
አሁን ግን ዐይኔ አየችህ።
[6]ስለዚህ ራሴን እንቃለሁ፤
በትቢያና በዐመድ ላይ ተቀምጬ ንስሓ
እገባለሁ።”

## *መደምደሚያ*

[7]*እግዚአብሔር* ይህን ለኢዮብ ከተናገረ በኋላ፣ ቴማናዊውን ኤልፋዝን እንዲህ አለው፤ “እንደ አገልጋዬ እንደ ኢዮብ ስለ እኔ ቅን ነገር ስላልተናገራችሁ፣ ቍጣዬ በአንተና በሁለቱ ባልንጀሮችህ ላይ ነዶአል። [8]አሁን እንግዲህ ሰባት ወይፈኖችና ሰባት አውራ በጎች ይዛችሁ ወደ አገልጋዬ ወደ ኢዮብ ሂዱ፤ የሚቃጠል መሥዋዕትም ስለ ራሳችሁ አቅርቡ። እንደ አሳፋሪ ተግባራችሁ እንዳላደርግባችሁ አገልጋዬ ኢዮብ ስለ እናንተ ይጸልያል፤ እኔም ጸሎቱን እቀበላለሁ፤ እንደ አገልጋዬ እንደ ኢዮብ ስለ እኔ ቅን ነገር አልተናገራችሁምና።” [9]ቴማናዊው ኤልፋዝ፣ ሹሐዊው በልዳዶስና ናዕማታዊው ሶፋር *እግዚአብሔር* እንደ ተናገራቸው አደረጉ፤ *እግዚአብሔርም* የኢዮብን ጸሎት ተቀበለ።

[10]ኢዮብ ለወዳጆቹ ከጸለየ በኋላ፣ *እግዚአብሔር* እንደ ገና አበለጸገው፤ ቀድሞ በነበረው ፈንታ ዕጥፍ አድርጎ ሰጠው። [11]ወንድሞቹና እኅቶቹ፣ ቀድሞም ያውቁት የነበሩ ሁሉ ወደ እርሱ መጡ፤ በቤቱም ከእርሱ ጋር ምግብ በሉ። እነርሱም ሐዘናቸውን ገለጡለት፤ *እግዚአብሔርም* ካመጣበት መከራ ሁሉ አጽናኑት፤ እያንዳንዳቸውም ጥሬ ብርና[a] የወርቅ ቀለበት ሰጡት።

[12]*እግዚአብሔርም* ከፊተኛው ይልቅ የኋለኛውን የኢዮብን ሕይወት ባረከ። እርሱም ዐሥራ አራት ሺህ በጎች፣ ስድስት ሺህ ግመሎች፣ አንድ ሺህ ጥማድ በሬዎች፣ አንድ ሺህ እንስት አህዮችም ነበሩት። [13]ደግሞም ሰባት ወንዶችና ሦስት ሴቶች ልጆች ነበሩት፤ [14]የመጀመሪያዋን ይሚማ፣ ሁለተኛዋን ቃሥያ፣ ሦስተኛዋንም አማልቶያስ ቂራስ ብሎ ሰየማቸው። [15]እንደ ኢዮብ ሴቶች ልጆች የተዋቡ ሴቶች በምድሪቱ ሁሉ አልተገኙም፤ አባታቸውም ከወንድሞቻቸው ጋር ርስት ሰጣቸው።

[16]ከዚህ በኋላ ኢዮብ አንድ መቶ አርባ ዓመት ኖረ፤ ልጆቹንና የልጅ ልጆቹን እስከ አራት ትውልድ ድረስ አየ። [17]በዚህ ሁኔታ አርጅቶ፣ ዕድሜ ጠግቦ ሞተ።

42፥5 መሳ13፥22፤ ኢዮ26፥14፤ኢሳ6፥5፤ ማቴ5፥8፤ሉቃ2፥30፤ ሮሜ10፥17፤ ኤፌ1፥17-18
42፥6 ዘፀ10፥3፤ዕዝ 9፥6፤ኢዮ2፥8፤6፥29፤ 34፥33፤40፥4፤ሕዝ 6፥9፤ሮሜ12፥3
42፥7 ቍ8፤ኢሱ 1፥7፤ኢዮ9፥15፤32፥3
42፥8 ቍ7፤ዘፍ 8፥20፤20፥7፤ዘኍ 23፥1፡29፤ኢዮ 1፥8፤22፥30፤ሕዝ 45፥23፤ያዕ5፥15-16፤1ዮሐ5፥16
42፥9 ዘፍ19፥21፤ 20፥17፤ኢዮ2፥11፤ ሕዝ14፥14
42፥10 ዘዳ30፥3፤ ኢዮ1፥3፤መዝ14፥7፤ 85፥1-3፤126፥5-6፤ ፊል2፥8-9፤ያዕ5፥11
42፥11 ዘፍ37፥35፤ ኢዮ19፥13
42፥17 ዘፍ15፥15

[a]11 ዕብራይስጡ፣ *ኬሲታ* ይላል፤ ኬሲታ የገንዘብ ዐይነት ነው፤ ግን ክብደቱና መጠኑ በትክክል አይታወቅም

*42፥5፤* እግዚአብሔርን የሰሙት ኢዮብ፣ የኢዮብ ሦስቱ ባልንጀሮች እንዲሁም ኤሊሁ ብቻ ነበሩ፤ ነገር ግን አሁን ኢዮብ እግዚአብሔርን አየ (ኢሳ 6፥5 ይመ)፤ ይህም በእምነት ዐይንና በመንፈሳዊ መረዳት ነው። ስለዚህ አሁን እግዚአብሔር ስለ ሕይወቱ ያለውን ዕቅድ (ቍ 2 ይመ) ሊቀበል ይችላል። *ዐይኔ አየችህ፤* በ19፥26 ላይ ለተሰጠው ተስፋ (ማብ ይመ) እንደ ቀዳሚ እጅ ገብ (ቀብድ) የሚቈጠር ነው።

42፥6 *ራሴን እንቃለሁ፤* የ9፥21 ማብ ይመ። ኢዮብ በእግዚአብሔር ላይ ስለ ተናገረው የድፍረት ቃል ራሱን ዝቅ በማድረግ (40፥4-5 ይመ) ንስሓ ይገባል። *በትቢያና በዐመድ፤* 30፥19 እና ማብ ይመ።

*42፥7-9፤* ኢዮብ በመከራው ጊዜ በቃልና በተግባር ቢበድልም፣ በእግዚአብሔር ፊት ሞገስ አገኘ፤ ወዳጆቹ ግን ተገሠጹ። ምክንያቱም በቀጣ ላይ ሳለና እግዚአብሔርን፣ “ለምን እንዲህ ይሆናል?” ባለበት ጊዜ እንኳን በእርሱ ፊት በቅንነት ለመናገር ቈርጦ ተነሥቶ ነበር። የኢዮብ አማካሪዎች ግን በቃላት ያሸበረቀ የተዋበ ሃይማኖታዊ ንግግር ቢያደርጉም እንኳ፣ እናከብረዋለን የሚሉትን አምላክ የሚያሳይ ሕያው ዕውቀት አልነበረበትም። ኢዮብ ከእግዚአብሔር ጋር ተነጋገረ፤ እነርሱ ግን ስለ እግዚአብሔር እናውቃለን በማለት ብዙ ሐሳብ አዥጎድጕደዋል፤ ከአጕል መንፈሳዊነትና ድፍረት የተነሣም የሌላቸውን ዕውቀት አለን እስከ ማለት ደርሰው ነበር። ኢዮብ ለምን እንደሚሠቃይም የሚያውቁ መሰላቸው።

42፥7-8 *አገልጋዬ... ኢዮብ፤* ይህ ሐረግ በዚህ ክፍል አራት ጊዜ ተጠቅሶአል።

*42፥10፤* ኢዮብ ስሙን ላጠፉት ሰዎች ያደረገው ጸሎት፣ ጌታችን በማቴ 5፥44 ላይ ለአስተማረው ትምህርት የክርስቲያን በጎ ሕይወት እንዴት መሆን እንዳለበት ለማሳየት ከብሉይ ኪዳን የሚጠቀስ ግሩም ማስረጃ ነው። ይህ የኢዮብ ጸሎት ኢዮብ ወደ ቀድሞ ሀብቱ ይመለስ ዘንድ አዲስ ምዕራፍ የከፈተ ነው። *እንደ ገና አበለጸገው፤* በመዝ14፥7 ላይ የዚህ ሐረግ የዕብራይስጥ ትርጕም፣ “የሕዝቡን ምርኮ በሚመልስበት ጊዜ” (መዝ 14፥7) የሚል ነው።

*42፥11፤* ከ16፥2፤ ከ19፥13 ጋር ያነጻጽሩ። *ጥሬ ብርና፤* በብሉይ ኪዳን ይህ ሐረግ የሚገኘው በዘፍ 33፥19 እና (በዚህ ቦታ ላይ የሚገኘውን ማብ ይመ) በኢሱ 24፥32 ላይ ብቻ ነው።

*42፥12-16፤* በሰይጣን ይካሄድ የነበረው ዓለም አቀፋዊው መንፈሳዊ ጦርነት አሁን አብቅቶአል፤ ኢዮብም ቀድሞ የነበረውን ጤንነት ከማግኘቱም በላይ አሁን ባለሙሉ ሀብት ሆኖአል፤ ከእንግዲህ ኢዮብ በሥቃይ ውስጥ ይገኝ ዘንድ አስፈላጊ የሚሆንበት ምክንያት የለም። እግዚአብሔር ያለምክንያት እንድ ንሠቃይ አይፈልግም፤ እኛ በዚህ ዓለም እያለን እርሱ በመለኮት ምስጢሩ ያመጣውን ሥቃይ ማስተዋል ባንችልም (ኢሳ 55፥8-9) እርሱ ምንጊዜም ትክክል የሆነውን ነገር እንደሚሠራ ማመን ይኖርብናል።

*42፥12፤* የኢዮብ የእንስሳት ሀብት በፊት ከነበረው (1፥3 ይመ) ይልቅ በዚህ ጊዜ በእጥፍ ጨምሮአል (ቍ 10 ይመ)።

42፥13 *ሰባት ወንዶችና ሦስት ሴቶች ልጆች፤* ከዚህ ቀደም የሞቱበትን ልጆች ለመተካት ነው (1፥2፡18-19 ይመ)።

42፥14 *ይሚማ፤* “ርግብ” ማለት ነው። *ቃሥያ፤* “ቀረፋ” ማለት ነው። *አማልቶያስ ቂራስ፤* “በቀላሉ ሊሰበሩ የሚችሉ ነገሮች ማስቀመጫ” ማለት ነው፤ ይህም እጅግ ተወዳጅ የሆነ የዐይን ቅባት ወይም ኵል ነው (ኤር 4፥30 ማብ ይመ)።

42፥15 *ከወንድሞቻቸው ጋር ርስት ሰጣቸው፤* ከዘኍ 27፥8 ጋር ያነጻጽሩ።

42፥16 *አንድ መቶ አርባ ዓመት ኖረ፤* የነገድ አባቶች ረጅም የዕድሜ ዘመን ነው (የዘፀ 6፥16 ማብ ይመ)። *እስከ አራት ትውልድ ድረስ አየ፤* ዘፍ 50፥23 ይመ።

42፥17 *አርጅቶ፣ ዕድሜ ጠግቦ፤* 5፥26 እና ማብ እንዲሁም ዘፍ 25፥8 ይመ።

# መጽሐፈ መዝሙር

## መግቢያ

### አሰያየሙ

“መዝሙራት” እንዲሁም “መጽሐፈ መዝሙር” የሚሉት ስያሜዎች የተወሰዱት ከሰፕቱዋጊንት (ከዕብራይስጥ ወደ ግሪክ ከተመለሰው ትርጒም) ላይ ሲሆን፣ እነዚህ ስያሜዎች በመጀመሪያ የአውታር መሣሪያዎችን (እንደ ክራር፣ መሰንቆና በገና የመሳሰሉትን) ቀጥሎም በልዩ ልዩ መሣሪያ ታጅበው የሚ ዘመሩትን መዝሙሮች ያመለክቱ ነበር:: ምንም እንኳ በመጽሐፈ መዝሙር ውስጥ የምናገኛቸው መዝ ሙሮች በአብዛኛው “ቴፊሎትም”(ጸሎቶች) ቢሆኑም፣ ሲወርድ ሲዋረድ በመጣው በዕብራውያን ልማድ ግን “ቴሒሊም”(“ውዳሴዎች”፤ የ145 ርእስ ማብ ይመ) የሚል ስያሜ ተሰጥቷቸዋል:: በመጽሐፉ ውስጥ ከተካተቱት ስብስቦች አንዱ “የእሴይ ልጅ የዳዊት ጸሎት” (72፥20) የሚል ርእስ የተሰጠው በዚህ ምክን ያት ነው::

### የመጽሐፉ አሰባሰብ፣ አቀነባበርና የተጻፈበት ጊዜ

መጽሐፈ መዝሙር የስብስቦች ስብስብ ከመሆኑም በላይ አሁን ባለው ደረጃ ሊዘጋጅ የቻለው በብዙ ምእተ ዓመታት ሂደት ውስጥ ነው :: መጽሐፉ አሁን ያለውን የመጨረሻ ገጽታ የያዘው ከምርኮ በኋላ በቤተ መቅደሱ ውስጥ ያገለግሉ በነበሩ ሹማምት ሲሆን፣ ይህም የሆነው በሦስተኛው ምእተ ዓመት ዓ.ቅ.ክ. ገደማ ነው:: መጽሐፉ የጸሎት መጽሐፍ (ማለትም የጸሎት፣ የውዳሴና የሃይማኖት መመሪያ መጽሐፍ) በመሆን በሁለተኛው (በዘሩባቤልና በሄሮድስ ዘመን) ቤተ መቅደስና በምኵራቦች ውስጥ ያገለግል ነበር:: በመጀመሪያው ምእተ ዓመት ላይ “መጽሐፈ መዝሙር ወይም የመዝሙር መጽሐፍ” በመባል ይታወቅ ነበር (ሉቃ20፥44፤ ሐሥ1፥20):: በዚያን ዘመን መዝሙራት የሚለው መጠ ሪያ በአይሁድ የብሉይ ኪዳን ቀኖና ውስጥ “ጽሑፎች” የሚል ርእስ የተሰጠውን ክፍል ይወክል ነበር:: ይህ መጽሐፍ በዚህ መልክ ተሰብስቦ ከመዘጋጀቱ በፊት በርካታ ስብስቦች ነበሩ:: እርግጥ መዝሙራቱ መሰብሰብና መዘጋጀት የጀመሩት በመጀመሪያው (የሰለሞን) ቤተ መቅደስ (ወይም በዳዊት ዘመን) በመጀመሪያ ዎቹ ዓመታት ላይ ሳይሆን አይቀርም፤ በቤተ መቅደሱ ውስጥ ሥርዐተ ቅዳሴ መልክና ቅርጽ እየያዘ የመጣውም በዚያን ጊዜ ነበር:: ከዚህ ጊዜ ጀምሮ “የዳዊት ጸሎቶች” የሚለው መጠሪያ የተለመደ ሆነ:: በዚህ መጽሐፍ ውስጥ እንዲካተቱ ከተደረጉት ሌሎች ስብስቦች ውስጥ የሚከተሉት ይገኙበታል፤ (1) የቆሬ ልጆች መዝሙር (መዝ42-49፤84-85፤87-88)፤(2) የአሳፍ መዝሙር (መዝ50፤73-83) እንዲሁም (3) የመዓርግ መዝሙር (መዝ120-134)::

መጽሐፉ በየጊዜው ከተሰበሰቡ መዝሙሮች የተዘጋጀ መሆኑን የሚጠቁሙ ሌሎች ማስረጃዎች አሉ:: መዝ1-41 (ክፍል አንድ) “ያህዌ” (እግዚአብሔር) የሚለውን ስመ እግዚአብሔር ብዙ ጊዜ ሲጠ ቀም፣ መዝ42-72 (ክፍል ሁለት) ደግሞ “ኤሎሂም” (“እግዚአብሔር /አምላክ”) የሚለውን ብዙ ጊዜ ይጠቀ ማል:: ይሁን እንጂ በክፍል ሁለት ውስጥ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶ የምናገኘው ስመ እግዚአብሔር (“ኤሎ ሂም”) በክፍል አንድ ውስጥ ተጠቅሶ ከምናገኘው (“ያህዌ”) ለምን እንደ ተለየ የተገለጸ ነገር የለም፤ የሆነ ሆኖ ሁለቱም ስሞች በእስራኤል ንጉሥ መንግሥ ከጀመረበት ጊዜ አንሥቶ የታወቁ መሆናቸውን መናገር ይቻላል:: ከዚህ በተጨማሪ መዝ93-100 ከእስራኤል ታሪክና እምነት ጋር ተያይዞ የተሰበሰበ ይመስላል (በ9፥31፤96፥10፤97፥1፤99፥1 ላይ “እግዚአብሔር ነገሠ” የሚለውን ይመ):: በተመሳሳይ ርእስ ዙሪያ የተጐዳኙ ሌሎች መዝሙሮችም አሉ፤ እነርሱም መዝ111-118 (“የግብፃውያን ሃሌል”)፣ መዝ 138-145 (በየመዝሙሮቹ ርእስ ላይ “የዳዊት” የሚል ቃል ተጠቅሶአል) እንዲሁም መዝ 146-150 (እግዚአብሔርን አመስግኑ የሚል ሐረግ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶአል) ናቸው:: “ታላቁ ሃሌል” (መዝ120-136) በመባል የሚታወቀው ክፍል ዕውቅና ይኑረው ወይም አይኑረው ምንም የሚታወቅ ነገር የለም:: (የሚጠ ሩበትን ስም ከክርስቲያኖች ሥርዐተ ቅዳሴ የወሰዱት ሰባቱ “የንስሓ መዝሙሮች” በአይሁድ የመዝሙ ራት ስብስብ ውስጥ እንደ አንድ ክፍል ተደርገው አይታዩም፤ የመዝ6 መግቢያን ይመ)::

መጽሐፈ መዝሙር 150 መዝሙሮችን ይዟል፤ ይህም የሆነው በልዩ ልዩ አርታዕያን ከተዘጋጀ በኋላ ነው:: የሰብዓ ሊቃናት ትርጒምና የዕብራይስጡ ቅጅ፣ መጽሐፉ 150 መዝሙሮች እንዳሉት ቢ ያመ ለክቱም ወደዚህ ቍጥር የሚደርሱት ግን በተለያየ መንገድ ነው:: ቍጥሩ ሲሰላ የሰብዓ ሉቃናት ትርጒም አንድ ተጨማሪ መዝሙር አለው (ሆኖም መዝ151 ብሎ በግልጽ አይጠቅስም)፤ እንዲሁም መዝ9-10 እና መዝ114-11 አንድ መዝሙር ሲያደርጋቸው፣ መዝ116 እና መዝ147ን እያንዳንዳ ቸውን ሁለት መዝሙሮች ያደርጋቸዋል:: እዚህ ላይ አንድ የሚያስደንቅ ነገር ይታያል፤ ይኸውም የሰብዓ ሊቃናቱ ትርጒምና የዕብራይስጡ ቅጅ መዝ 42-43 እንደ ሁለት መዝሙሮች አድርገው ይወስዷቸ ዋል፤ በመሠረቱ ግን አንድ መዝሙር ናቸው::

መጽሐፈ መዝሙር በአምስት መጻሕፍት ይከፈላል (መዝ1-41፤42-72፤73-89፤90-106፤107-150)፤ እያንዳንዱ መጽሐፍ የሚያበቃው በቃለ ውዳሴ ነው (41፥13፤ 72፥18-19፤ 89፥52፤ 106፥48፤150 ይመ):: ቀደም ሲል እንደ ተመለከተው፣ የመጀመሪያዎቹ ሁለት መጻሕፍት ቅድመ ምርኮ ሳይሆኑ አይቀርም:: የተቀረው መዝሙር በሦስት መጻሕፍት የተከፈለውና በድምሩ አምስት መጻሕፍት እንዲሆኑ የተደረ

ገው ምናልባት ከአምስቱ የሙሴ መጻሕፍት ጋር እንዲመሳሰል ለማድረግ ነው:: ከእነዚህ ክፍፍሎች (በመዝ106 እና 107 መካከል) ውስጥ አንዱ ቢያንስ በኋሊብ የተደረገ ነው (የመዝ 107 መግቢያ ይመ):: መጽሐፉ በአምስት ከመከፈሉ በስተቀር እንደ አንድ መጽሐፍ ሊታይ ስለሚችል፣ የራሱ መግቢያና (መዝ 1-2) መደምደሚያ (መዝ146-150) አለው:: በመዝሙሩ ውስጥ የሚገኙት ማብራሪያዎች መዝሙሩ በዚህ መልክ ሊከፈል ስለቻለበት ምክንያት ተጨማሪ ሐሳብ ይሰጣሉ::

## ጸሓፊውና አርእስቶቹ

ከ150 መዝሙራቱ መካከል ርእስ የሌለው መዝ34 ብቻ ነው (በሰብዓ ሊቃናት ትርጒም ላይ ደግሞ መዝ17 ብቻ ነው):: እነዚህ በተለምዶ "ባለቤት /ወላጅ የለሽ መዝሙራት" በመባል የሚታወቁት በአብዛኛው የሚገኙት ከመጽሐፍ 3-5 ባሉት ክፍል ነው፤ የሚገኙትም ችምችም ብለው ነው (መዝ91፤93፤97፤99፤104፤107፤111፤119፤135፤137፤146፤150):: በመጽሐፍ 1 እና 2 ውስጥ ርእስ የሌላቸው መዝ12፤10፤33፤43፤71 ናቸው፤ እርግጥ መዝ 10 እና 43 ተከታይ መዝሙሮች ናቸው:: የርእሶቹ ይዘት ቢለያይም በጥቅሉ ግን ከዚህ እንደሚከተለው ሊመደቡ ይችላሉ፤ እነዚህም (1) ጸሓፊ፣ (2) የሰብሳቢው (የአካቢው) ስም፣ (3) የመዝሙሩ ዐይነት፣ (4) የሙዚቃ (የዜማ) ምልክቶች፣ (5) ሥርዐተ ቅዳሴዎች፣ (6) የመዝሙራቱ ዐላማ ናቸው:: ለዝርዝር ማብራሪያ በየመዝሙሮቹ መግቢያ ላይ የሚገኙትን ርእሶች ይመ::

መጽሐፉን በጥልቀት ለማጥናት የሞከሩ ሰዎች በርእሶቹ ጥንታዊነትና ተዓማኒነት ላይ አልተስማሙም:: ብዙዎቹ ርእሶች ቅድመ ምርኮ በመሆናቸው፣ የሰብዓ ሊቃናት ተርጓሚዎች እንኳ ትርጒማቸውን በውል ሊያውቁት አልቻሉም:: ከዚህም በላይ የጸሓፊውን ስምና ርእስ ከጽሑፉ ጋር አያይዞ ማቅረብ በጥንት ዘመን የተለመደ ነበር:: በሌላ በኩል ደግሞ በሰብዓ ሊቃናቱ ትርጒምና በዕብራይስጡ ቅጆች መካከል የተደረጉ ንጽጽሮች እንደሚያሳዩት፣ በርእሶቹ መካከል ልዩነት አለ:: የምሁራኑ ውይይት የሚያተኩረው ከፍ ሲል በተጠቀሱት በተራ ቍጥር 1 እና 6 ላይ ነው::

መዝሙራቱ የተደረሱበትን ጊዜ የሚያመለክቱት ርእሶች የተጻፉት ከ1ኛና 2ኛ ሳሙኤል መጻሕፍት ላይ እንደተወሰዱ ተደርገው ነው:: በተጨማሪም ርእሶቹ ከመዝሙራቱ ይዘት ጋር አይጣጣሙም:: ይህም አንድ ጥርጥጣሬ አስከትሏል፤ ይኸውም ለመዝሙራቱ ርእስ የተሰጣቸው ከሰዎች ሕይወት ታሪክ ጋር ለማስማማት ታስቦ ነው:: ይሁንና የምልክቶቹ ቍጥር ውሱን የሆነው ለምንድን ነው? የመዝሙራቱስ ርእስ ከይዘቱ ጋር ያልተጣጣመው ለምንድን ነው? ውይይቱ በሁለቱም አቅጣጫ ይሄዳል::

የመዝሙሩን ጸሓፊም በተመለከተ የተለያዩ አስተያየቶች ተሰጥተዋል:: ምልክቶቹም ቢሆኑ አከራካሪ ናቸው:: ምክንያቱም ይህን ለመግለጽ የገቡት ሐረጎች በሙሉ ጥቅል እንጂ ዝርዝር ሐሳብ የላቸውም:: ስሞቹ የሚያመለክቱት መዝሙራቱ የተሰበሰቡት በተወሰኑ ሰዎች መሆናቸውን ነው ("የአሳፍ" ወይም "የቆሬ ልጆች"):: የመዝሙሩ ጸሓፊ ዳዊት ነው የሚለው አመለካከት ብዙ ችግር ባያኖርበትም፣ መጽሐፉ በአንድ ወቅት ዝነኛ ዘማሪና ሙዚቀኛ የነበረውን ሰው መዝሙሮች ይዟል:: መዝሙሮቹ ስለ ዳዊት ወይም ከዳዊት ቤት ስለሚወጡት ንጉሦች ያትታሉ::ይሁንና የትኞቹ መዝሙሮች በዳዊት እንደ ተጻፉ በትክክል መናገር አይቻልም:: በዳዊት እንደ ተጻፉ የሚነገርላቸው መዝሙሮችም ቢሆኑ ከዳዊት በኋላ ስላለው ዘመን የሚያወሱ ናቸው (ለምሳሌ የመዝ30 ርእስ፤ የመዝ69 መግቢያንና የመዝ122 ርእስ ይመ):: ከዚህ በተጨማሪ በርእሶቹ ላይ ገብቶ የምናገኘው "ዳዊት" የሚለው ስም ከእርሱ ቤት የሚወጡትን ነገሥታት ያመለክታል::

"ሴላ" የሚለው ቃል የሚገኘው በ39 መዝሙሮች ላይ ነው:: ከሁለቱ በስተቀር (መዝ 140፤143፤ ሁለቱም በዳዊት የተጻፉ ናቸው) የተቀሩት በሙሉ የሚገኙት በመጽሐፍ 1-3 ላይ ነው:: ይህ ቃል በዕንባቆም 3 ላይ ይገኛል:: የቃሉን ትርጒም በተመለከተ ብዙ አስተያየቶች ቢኖሩም፣ እንደ እውነቱ ከሆነ ግን ምንም የሚታወቅ ነገር የለም:: ምናልባት የሥርዐተ ቅዳሴ ምልክት ሊሆን ይችላል:: ባንጻሩም ቃሉ በዕብራይስጡ ቅጂ ላይ ስለ መገኘቱ አጠያያቂ ነው::

## የመዝሙራቱ ዐይነት

የመዝሙራቱ ርእሶች በጥንት ጊዜ የነበረውን የአከፋፈል ሥርዐት እንድናስተውል ይረዱናል:: እነዚህም፣ (1) ሚዝሞር ("መዝሙር")፤ (2) ሺጋዮን (የመዝ7 ርእስ ማብ ይመ)፤ (3) ሚክታም (የመዝ 16 ርእስ ማብ ይመ)፤ (4) ሺር ("ዝማሬ")፤ (5) ማስኪል (የመዝ32 ማብ ይመ)፤ (6) ቴፊላህ ("ጸሎት")፤ (7) ቴሂላህ ("ምስጋና")፤ (8) ሌሃዝክሪ ("በእግዚአብሔር ፊት ለመታሰብ የሚቀርብ ምስጋና")፤ (9) ሌቶዳህ ("ውዳሴ" ወይም "ምስጋና")፤ (10) ሌላሜድ ("ትምህርት")፤ (11) ሺር የዲዶት ("የፍቅር መዝሙር" ማለት በሠርግ ላይ የሚዘመር) ናቸው:: የእነዚህ ስያሜዎች ትርጒም ግን በትክክል አይታወቅም::

የመዝሙራቱን ይዘት በዝርዝር ያጠኑ ሰዎች መዝሙራቱን በተለያዩ ፈርጆች ለመመደብ ተገደዋል፤ ይህም መዝሙራቱን አመቺ በሆነ መንገድ ለማጥናት በር ከፍቷል:: ዋና ዋናዎቹ የመዝሙሮች ዐይነት ከዚህ የሚከተሉት ናቸው፤ (1) የግለ ሰቦች ጸሎት (መዝ3፤7-8)፤ (2) እግዚአብሔር ማዳኑን ያሳያቸው ግለ ሰቦች/ያቀረቡት ምስጋና (መዝ30፤34)፤ (3) የኅብረተ ሰቡ ጸሎት (መዝ12፤44፤79)፤ (4) እግዚአብሔር ማዳኑን ያሳያቸው ኅብረተ ሰቦች ያቀረቡት ምስጋና (መዝ66፤75)፤ (5) በእግዚአብሔር የሚታመን ሰው የተናገረው ቃል (መዝ11፤16፤52)፤ (6) የእግዚአብሔርን ታላቅነትና በጎነት ለመወደስ

የቀረበ መዝሙር (መዝ8፤19፤29፤65)፤ (7) እግዚአብሔር በመላው ዓለም መንገሡን የሚያውጅ መዝሙር (መዝ47፤93-99)፤ (8) የእግዚአብሔር ከተማ የጽን መዝሙር (መዝ46፤48፤76፤ 84፤ፃ22፤126፤129፤137)፤ (9) እግዚአብሔር ስለ ቀባው ንጉሥ የቀረበ ንጉሣዊ መዝሙር (መዝ2፤18፤20፤ 45፤72፤89፤110)፤ (10) የተሳላሚዎች መዝሙር (መዝ120-134)፤ (11) የቅዳሴ መዝሙር (መዝ15፤24፤68)፤ (12) የትምህርት መዝሙር (1፤34፤37፤73፤112፤119፤128፤133)።

ይህ አፈራረጅ ራሱ ተወራራሽ ነው። ለምሳሌ "የግለ ሰቦች ጸሎት" የተባለው የንጉሡን ጸሎት ወይም የኅብረተ ሰቡን ጸሎት ሊያካትት ይችላል። ይሁንና ተመሳሳይ ይዘት ያላቸውን መዝሙሮች ጐን ለጐን ማጥናት የራሱ የሆነ ጠቀሜታ አለው። መዝሙራቱ የሚዘመሩበት ቀን አላቸው የሚለው አመለካከት ግን ይሄን ያህል አሳማኝ አይደለም። በዚህ ረገድ የተሰጠውን ማብራሪያ በየመዝሙራቱ መግቢያ ላይ ይመ።

ከእነዚህ መዝሙሮች ውስጥ የጸሎት መዝሙሮች (በግለ ሰቦችም ሆነ በኅብረተ ሰቡ የቀረቡት) እጅግ ውስብስብ ናቸው። መዝሙረኛው አቤቱታውን ለእግዚአብሔር የሚያቀርበው በተለያዩ ቋንቋዎች ነው፤ (1) ወደ እግዚአብሔር በመጮኽ፤ "እግዚአብሔር ሆይ"፣ "አምላኬ ሆይ"፣ "አዳኜ"፤ (2) አቤቱታውን በመደርደር፤ "ተነሥ"፣ "መልስልኝ"፣ "እርዳኝ"፣ "ታደገኝ"፤ (3) ጭንቀቱን በመግለጽ፤ "ብዙዎች ተነሥተውብኛል"፣ "ክፉዎች አሳደውኛል"፣ "ተጨንቄአለሁ"፤ (4) በእግዚአብሔር ላይ ያለውን ጥያቄ በመናገር፤ "ስለ ምን ተውኸኝ"፣ "ፊትህን ከእኔ የምትሰውረው እስከ መቼ ነው"፤ (5) ይግባኙን በማስታወቅ፤ "ከእኔ አትራቅ"፣ "ፍረድልኝ"፤ (6) እግዚአብሔር ልመናውን እንዲያደምጥ በማድረግ፤ "መሸሸጊያዬ አንተ ነህ"፣ "ስለ ስምህ ብለህ"፤ (7) በባላጋራዎቹ ላይ ክሱን በማቅረብ፤ "በአፋቸው እውነት የለም"፣ "ጨካኝ ሰዎች ነፍሴን ተመኙ"፤ (8) እግዚአብሔር ጠላቶቹን እንዲበቀልለት በመለመን፤ "ይዋረዱ"፤ (9) ንጽሕናውን በማስታወቅ፤ "በጽድቅ ተመላለስሁ"፣ "ያለ ምክንያት ጠሉኝ"፤ (10) ኀጢአቱን በመናዘዝ፤ "አንተን በድያለሁ"፣ "በደሌን እናዘዛለሁ" (11) እምነቱን በመግለጽ፤ "አንተ ጋሻዬ ነህ"፣ "አንተ ትመልስልኛለህ"፤ (12) እግዚአብሔር የሚታደገው ከሆነ ምስጋና ለማቅረብ ቃል በመግባት፤ "ስለ ኀይልህ እዘምራለሁ"፣ "ከንፈሮቼ ያመሰግኑሃል"፤ (13) ውዳሴ በማቅረብ፤ "እግዚአብሔርን ከእኔ ጋር ከፍ ከፍ አድርጉ"፣ "እግዚአብሔርን አመስግኑ"፤ (14) የሚያመሰግንበትን ምክንያት በመግለጽ፤ "ታድገኸኛልና"፣ "እግዚአብሔር የምስኪኖችን ጸሎት ይሰማል"።

ምንም እንኳ በሚቀርቡት ጸሎቶች ሁሉ ውስጥ እነዚህ ሁሉ ነገሮች ይታያሉ ለማለት ባያስደፍርም፣ ሁሉም ግን የአቤቱታ ጸሎቶች አካል ናቸው። በጥቅሉ የሚያሳዩን የፍርድ ቤት ገጽታን ነው። መዝሙረኛው አቤቱታውን በሰማያዊው ንጉሥ ዳኛ ፊት ያቀርባል። ክፉዎች ጠላቶች ሲያስጨንቁት፣ ያለበትን ሁኔታ በማስታወቅ ንጽሕናውን ይናገራል፤ ከዚያም እግዚአብሔር ጠላቶቹን እንዲበታትንለትና ቅን ፍርዱንም እንዲሰጠው ይለምናል። በእግዚአብሔር እጅ መከራ ሲደርስበት (እግዚአብሔር ባላጋራው ሲሆን)፣ ኀጢአቱን ይናዘዛል፤ ምሕረትም ይጠይቃል። በጸሎቶቹ ውስጥ የተጠቀሱትን የተለያዩ ንግግሮችና የፍርድ ውሳኔዎች ልብ ብሎ መመልከት ተደራስያን መዝሙሩን ይበልጥ እንዲረዱ ያግዛቸዋል።

### ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ

ምንም እንኳ በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ብዙ ጸሎቶች ቢገኙም፣ መዝሙሩ ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ የተጻፈው ግን በግጥም መልክ ነው፤ በብሉይ ኪዳን ውስጥ የሚገኙ ጸሎቶች ሁሉ የተጻፉት በግጥም መልክ አይደለም (1ነገ8፥23-53፤ ዕዝ9፥6-15፤ ነህ9፥5-37፤ ዳን9፥4-19 ይመ)። ወይም ደግሞ የውዳሴ ቃሎች ሁሉ የተጻፉት በግጥም መልክ አይደለም (1ነገ8፥15-21 ይመ)። መዝሙራቱ ልብ የሚነኩ፣ ምስል የሚከስቱና ሐሳብ የሚጨብጡ ናቸው። በምስል፣ በተነጻጻሪ ዘይቤና በተለዋጭ ዘይቤ የተሞሉ ናቸው። በተመሳሳይ ድምፅ የሚጨረሱ ወይም የሚጀምሩ ስንኞችን ማግኘት የተለመደ ነው። ቃልን ወይም ሐሳብን መድገምና ተመሳሳይ ትርጒም ያላቸውን ቃላት አንዱን በአንዱ ላይ መከመር ሌላው ባሕርያቱ ናቸው። ቁልፍ ቃላት በጸሎቱ ወይም በመዝሙሩ ውስጥ የሚገኙትን ዐበይት ጭብጦች የሚያጎለምሱ ናቸው። እያንዳንዱ መዝሙር የተቀነበበው በመግቢያውና በመደምደሚያው ላይ በሚገኙ ተመሳሳይ ቃላት ነው።

የዕብራይስጥ ግጥሞች ቤት አይመቱም። የግጥሞቹ ዐቢይ ባሕርይ ጒድኝት ነው። የግጥሙ ስንኞች ሁለት (አንዳንድ ጊዜ ሦስት) እኩል (ተመጣጣኝ) ክፍል አላቸው። ሁለተኛው ክፍል የመጀመሪያውን ክፍል በተመሳሳይ ጒድኝት የሚያስተገባ ወይም በተቃርኖ ጒድኝት የሚያነጻጽር ነው። እነዚህ ጒድኝቶች ጥቅል እንጂ በሁለቱ መሠረታዊ ስንኞች ውቅር ውስጥ ባለቅኔው ሊያሳይ የሞከራቸውን ልዩ የአገላለጽ ስልቶች ሙሉ በሙሉ የሚገልጹ አይደሉም። ይሁንና አንባቢው ልዩነቶቹን ለማወቅ እንዲችል ይረዱታል።

የዕብራይስጡ ግጥም ስንኞች (ወይም የስንኝ ክፍሎች) የሚጀምሩትና የሚጨርሱት የት እንደ ሆነ በትክክል መለየት አይቻልም። የሰብዓ ሊቃናቱ ትርጒም እንኳ ስንኞቹን የሚጀምረውና የሚጨርሰው ከዕብራይስጡ በተለየ መንገድ ነው። እንግዲህ ዘመናዊ ትርጒሞች ቢለያዩ የሚያስደንቅ አይደለም።

ከዚህ ጋር የሚያያዘው ችግር የዕብራውያን ባለ ቅኔዎች የአጻጻፍ ዘዬ በጣም አጭርና አንድ ወይም ሁለት ቃላትን በማጓደፍ ላይ የተመሠረተ መሆኑ ነው። የቃላቱን አገባብና ዝምድና የምናው

[8]እግዚአብሔር ቸር መሆኑን ቀምሳችሁ እዩ፤
እርሱን መጠጊያ የሚያደርግ ምንኛ ቡሩክ ነው!
[9]እናንተ ቅዱሳኑ፣ እግዚአብሔርን ፍሩት፤
እርሱን የሚፈሩት አንዳች አያጡምና።
[10]አንበሶች ሊያጡ፣ ሊራቡም ይችላሉ፤
እግዚአብሔርን የሚሹ ግን መልካም ነገር አይጐድልባቸውም።
[11]ልጆቼ ሆይ፣ ኑ፤ ስሙኝ፤
እግዚአብሔርን መፍራት አስተምራችኋለሁ።
[12]ሕይወትን የሚወድ፣
በጎውንም ያይ ዘንድ ዕድሜን የሚመኝ ማን ነው?
[13]አንደበትህን ከክፉ ነገር ከልክል፤
ከንፈርህንም ከሽንገላ ጠብቅ።
[14]ከክፉ ሽሽ፤ መልካሙንም አድርግ፤
ሰላምን ፈልጋት፤ ተከተላትም።
[15]የእግዚአብሔር ዐይኖች ወደ ጻድቃን ናቸው፤
ጆሮዎቹም ለጩኸታቸው ክፍት ናቸው።
[16]መታሰቢያቸውን ከምድር ለማጥፋት፣
የእግዚአብሔር ፊት በክፉ አድራጊዎች ላይ ነው።
[17]ጻድቃን ሲጮኹ፣ እግዚአብሔር ይሰማቸዋል፤
ከመከራቸውም ሁሉ ያድናቸዋል።
[18]እግዚአብሔር ልባቸው ለተሰበረ ቅርብ ነው፤
መንፈሳቸው የተሰበረውንም ያድናቸዋል።
[19]የጻድቅ መከራው ብዙ ነው፤
እግዚአብሔር ግን ከሁሉም ያድነዋል።
[20]ዐጥንቶቹን ሁሉ ይጠብቃል፤
ከእነርሱም አንድ አይሰበርም።
[21]ኀጢአተኞችን ክፋት ይገድላቸዋል፤
ጻድቃንን የሚጠሉ ይፈረድባቸዋል።
[22]እግዚአብሔር የባሪያዎቹን ነፍስ ይቤዣል፤
እርሱንም መጠጊያ ያደረገ አይፈረድበትም።

34፥8 መዝ2፥12፤ ዕብ6፥5፤1ጴጥ2፥3
34፥9 ዘዳ6፥13፤ መዝ23፥1፤ራእ14፥7
34፥10 መዝ23፥1
34፥11 መዝ19፥9፤ 32፥8፤66፥16
34፥12 መክ3፥13
34፥13 መዝ12፥2፤ 39፥1፤141፥3፤ምሳ13፥3፤21፥23፤ያዕ1፥26፤ 1ጴጥ2፥22
34፥14 መዝ37፥27፤ኢሳ1፥17፤ሮሜ14፥19፤3ዮሐ1፥11
34፥15 ኢዮ23፥10፤ 36፥7፤መዝ33፥18፤ ሚል3፥16፤ዮሐ9፥31
34፥16 ዘፀ17፥14፤ ዘሌ17፥10፤መዝ9፥6፤ ኤር23፥30፤1ጴጥ 3፥10-12
34፥17 መዝ145፥19
34፥18 ዘጸ4፥7፤ መዝ51፥17፤109፥16፤ 119፥151፤145፥18፤1 47፥3፤ኢሳ50፥8፤ 61፥1
34፥19 ቍ17፤ኢዮ 5፥19፤መዝ25፥17፤2 ጢሞ3፥11
34፥20 ዮሐ19፥36
34፥21 መዝ7፥9፤ 9፥16፤11፥5፤37፥20፤ 73፥27፤94፥23፤106፥ 43፤112፥10፤140፥11 ፤ምሳ14፥32፤24፥16
34፥22 ዘፀ6፥6፤ 15፥13፤መዝ2፥12፤ ሉቃ1፥68፤ራእ14፥3

## መዝሙር 35

### የተጨቈነ ሰው ጸሎት

የዳዊት መዝሙር

[1]እግዚአብሔር ሆይ፣ የሚታገሉኝን ታገላቸው፤
የሚዋጉኝንም ተዋጋቸው።
[2]ትልቁንና ትንሹን ጋሻ ያዝ፤
እኔንም ለመርዳት ተነሥ።
[3]በሚያሳድዱኝ ላይ፣
ጦርና ጭሬ ምዘዝ፤*

35፥1 ዘፀ14፥14፤1ሳሙ24፥15
35፥2 ዘፍ50፥24፤ኢዮ17፥3፤መዝ3፥3፡7

*3 ወይም ... መንገድ ዝጋ

የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም፤ እነዚህም መላእክት "የሚድኑትን ለማገልገል የሚላኩ አገልጋይ መናፍስት ናቸው" (ዕብ1፥14 ይመ፤ ደግሞም ከዘፍ32፥1-2፤ 2ነገ6፥17 ጋር ያነጻጽሩ)፤ እግዚአብሔር ቅዱሳኑን ከሥጋዊና ከመንፈሳዊ ጉዳት ለመጠበቅና ለማዳን መላእክቱን ሾሞአል።

*34፥8-14፤* "እግዚአብሔርን መፍራት" ተገቢ መሆኑን የሚያስተምር ክፍል ነው። የዕብራይስጥ ጸሐፊዎች ብዙውን ጊዜ ቁልፍ የሆነውን ሐሳብ የሚያስፍሩት በመካከል ላይ ነው (የ6፥6 ማብ ይመ)። ለምሳሌ በትእዛዝ አንቀጽ የሰፈሩትን ቃላት "ቅመሱ" (ቍ8)፤ "ፍሩ" (ቍ9)፤ "ኑ" (ቍ11)፤ "ጠብቅ" (ቍ13)፤ "ተለይ" (ቍ14) ልብ ብሎ መመልከት ይቻላል። በአንጓውም ላይ ጐልቶ የሚታየው "ቸር" የሚለው ሐሳብ ነው፤ ጌታ ቸር በመሆኑ (ቍ8) በእርሱ የሚታመኑት ሁሉ የሚያጡት አንዳች በጎ ነገር የለም (ቍ10)፤ ነገር ግን በጎ ዘመናትን ለማየት (ቍ12) ከክፉ መራቅና መልካምም ነገር ማድረግ ይኖርባቸዋል (ቍ14)፤ ማመንና መታዘዝ ማለት "እግዚአብሔርን" መፍራት ማለት ነው። የዚህን አንጓ ትምህርት ለማጤን መዝ37 ይመ፤ ሐዋርያው ጴጥሮስ በቍ12-16 ያለውን ሐሳብ በመልእክቱ ውስጥ እንዴት እንደ ተጠቀመበት ለማስተዋል 1ጴጥ3፥8-12 ይመ።

34፥8 *ቡሩክ፤* የ1፥1 ማብ ይመ።

34፥9 *ቅዱሳኑ፤* የ4፥3 ማብ ይመ። *እግዚአብሔርን ፍሩ፤* ቍ11 እንዲሁም የ15፥4 ማብ ይመ።

34፥11 *ልጆቼ ሆይ፤ ኑ፤* በጥበብ መምህራን ዘንድ የተለመደ አባባል ነው (ከመጽሐፈ ምሳሌ መግቢያ "ዐላማውና ትምህርቱ" የሚለውን ይመ)።

*34፥13፤* 15፥2-3፤ ያዕ3፥5-10 ይመ። ምላስ መሣሪያ ስለ መሆኑ የ5፥9 ማብ ይመ።

34፥14 *ሰላምን ፈልጋት፤* 37፥37፤ 120፥7፤ ምሳ12፥20፤ ዘካ8፥19 (እንዲሁም ዘካ8፥16-17 ይመ)፤ ማቴ5፥9፤ ሮሜ12፥18፤ 1ቆሮ7፥15፤ 2ቆሮ13፥11፤ 1ተሰ5፥13፤ ዕብ12፥14፤ ያዕ3፥17-18 ይመ።

*34፥15-18፤* እግዚአብሔር የጻድቃንን ጸሎት እንደሚሰማ የሚያረጋግጥ ነው። ክፉዎችን ግን ጨርሶ እስኪረሱ ድረስ ድራሻቸውን ያጠፋል (ቍ16)።

34፥15 *ጻድቃን፤* ቍ8-14፤ እንዲሁም የ1፥5 ማብ ይመ።

34፥16 *የእግዚአብሔር ፊት፤* የ13፥1 ማብ ይመ።

*34፥17-18፤* በተለይ 51፥17ን ይመ።

*34፥19-22፤* እግዚአብሔር የጻድቃን የዘላለም ታዳጊ መሆኑን የሚያረጋግጥ ነው፤ በጻድቃን ላይ የሚነሱ ክፉዎችን ግን እየተከታተለ (እያሳደደ) ያጠፋቸዋል (ቍ21 ይመ)።

34፥20 *ዐጥንቶቹን ሁሉ፤* ሁለንተናውን ማለት ነው (የ6፥2 ማብ ይመ)። *ከእነርሱም አንድ አይሰበርም፤* ከሁሉ በላይ "ጻድቅ የሆነውን" ጌታ ለማመልከት ምናልባት የዮሐንስ ወንጌል ጸሐፊ ይህንን አገላለጽ ሳይጠቀምበት አይቀርም።

34፥21-22 *ይፈረድባቸዋል፤* በበደላቸው ፍርድን ይቀበላሉ ማለት ነው።

34፥22 *ይቤዣል፤* የ25፥22 ማብ ይመ።

*መዝሙር 35፤* ለማያዊ ንጉሥ መለኮታዊ ጠረኛና ዳኛ በመሆኑ "የአገልጋዩን" (ቍ27) ስም ፍቅሩንና ወዳጅነቱን የገለጠላቸው ሰዎች እያጠፉት ስለሆነ ከዚህ ሁሉ ክፋት ተሟግቶ እንዲታደገው የቀረበ አቤቱታ ነው። ጠላቶች ያደረሱበት ጥቃትም በንጉሡ ላይ (ቍ15:19:21:25 ይመ) ጭንቀት (ቍ26) ሳያመጣበት አልቀረም፤ ምናልባትም ሕመም አምጥቶበት ሊሆን ይችላል (ቍ13፤ እንዲሁም የመዝ6 መግቢያን ይመ)። በመዝ34፥15-22 ላይ መዝሙረኛው ንጹሕ መሆኑን እንዳመለከተው ሁሉ በዚህም ቦታ ከበደል ነጻ መሆኑንና ጌታም ይህንን ንጽሕናውን ያስታውቅለት ዘንድ ጩኸቱን ሲያሰማ ይታያል፤ በሁለቱ ምዕራፎች መካከል ልዩነት ቢኖር በዚህ ቦታ መዝሙረኛው ራሱን "ጻድቅ" ብሎ አለመጥራቱ ነው (34፥21)። ወደ መዝሙሩ አወቃቀር ስንመጣ፣ መዝሙረኛው አቤቱታውን ለመለኮታዊው ጠረኛ ካሰማ በኋላ (ቍ1-3) ለመለኮታዊው ዳኛ ያቀረበውን አቤቱታ በሦስት እጅ እያሰረና እያብራራ ያቀርባል፤ እያንዳንዱም ክፍል የሚያበቃው የምስጋና መሥዋዕት ለማቅረብ ቃል በመግባት ነው (ቍ4-10:11-18:19-28)፤ እንዲሁም የ7፥17 ማብ ይመ።

*35፥1-3፤* ጠረኛና ንጉሥ ለሆነው ጌታ የቀረበ አቤቱታ ነው (ዘፀ15፥1-8 ይመ) ምክንያቱም ዳዊት ያለ አግባብ እየተበደለና እየተጨቈነ ነው።

35፥2 *ተነሥ፤* የ3፥7 ማብ ይመ።

ነፍሴንም፣ "የማድንሽ እኔ ነኝ" በላት።

[4]ሕይወቴን የሚፈልጓት፣
ይቅለሉ፣ ይዋረዱ፤
እኔን ለማጥፋት የሚያሤሩ፣
አፍረው ወደ ኋላቸው ይመለሱ።

[5]በነፋስ ፊት እንዳለ እብቅ ይሁኑ፤
*የእግዚአብሔር* መልአክ ያሳዳቸው።
[6]መንገዳቸው ጨለማና ድጥ ይሁን፤
*የእግዚአብሔር* መልአክ ያባርራቸው።
[7]ያለ ምክንያት ወጥመዳቸውን በስውር
አስቀምጠውብኛልና፤
ያለ ምክንያት ለነፍሴ ጕድጓድ
ቈፍረውላታል።
[8]ያልታሰበ ጥፋት ይምጣባቸው፤
የሰወሩት ወጥመድ ይያዛቸው፤
ይጠፉም ዘንድ ወደ ጕድጓዱ ይውደቁ።
[9]ነፍሴም *በእግዚአብሔር* ደስ ይላታል፤
በማዳኑም ሐሤት ታደርጋለች።
[10]የሥራ አካላቴ እንዲህ ይልሃል፤
"*እግዚአብሔር* ሆይ፤ እንደ አንተ
ማን አለ?
ድኻውን ከእርሱ ከሚበረቱ፣
ችግረኛውንና ምስኪኑን ከቀማኞች
ታድናለህ"።

[11]ጨካኝ ምስክሮች ተነሡ፤
ስለማላውቀውም ነገር ጠየቁኝ።
[12]በበጎ ፈንታ ክፉ መለሱልኝ፤
ነፍሴንም ብቸኛ አደረጓት።
[13]እኔ ግን እነርሱ በታመሙ ጊዜ
ማቅ ለበስሁ፤
ነፍሴንም በጾም አደከምኋት፤
ጸሎቴም መልስ አጥቶ ወደ ጕያዬ
ተመለሰ።

[14]ለወዳጄ ወይም ለወንድሜ እንደማደርግ፣
እየተንቈራጠጥሁ አለቀስሁ፤
ለእናቴም እንደማለቅስ፣
በሐዘን አንገቴን ደፋሁ።
[15]እነርሱ ግን እኔ ስሰናከል በእልልታ
ተሰበሰቡ፤
ግፈኞች በድንገት ተሰበሰቡብኝ፤
ያለ ዕረፍትም ቦጨጨቁኝ።
[16]እንደ ምናምንቴዎች አፌዙብኝ፤[ɣ]
ጥርሳቸውንም አፋጩብኝ።
[17]ጌታ ሆይ፤ እስከ መቼ ዝም ብለህ
ታያለህ?
ነፍሴን ከክፉ ሥራቸው፣
ብርቅ ሕይወቴን ከአንበሶች ታደጋት።
[18]በታላቅ ጉባኤ መካከል አመሰግንሃለሁ፤
ብዙ ሕዝብ በተሰበሰበበትም
አወድስሃለሁ።

[19]ከምድር ተነሥተው ጠላቶቼ የሆኑት፣
በላዬ ደስ አይበላቸው፤
እንዲያው የሚጠሉኝ፣
በዐይናቸው አይጣቀሱብኝ።
[20]የሰላም ንግግር ከአፋቸው አይወጣም፤
ዳሩ ግን በምድሪቱ በጸጥታ በሚኖሩት
ላይ፣
ነገር ይሸርባሉ።
[21]አፋቸውን አስፍተው ከፈቱብኝ፤
"እሰይ! እሰይ! በዐይናችን አየነው" አሉ።

[22]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ይህን አይተሃልና
ዝም አትበል፤
ጌታ ሆይ፤ ከእኔ አትራቅ።
[23]አምላኬ፣ ጌታዬ፤ ለእኔ ለመሟገት ተነሥ!
ልትከራከርልኝም ተንቀሳቀስ።
[24]*እግዚአብሔር* አምላኬ ሆይ፤ በጽድቅህ
ፍረድልኝ፤
በእኔም ላይ ደስ አይበላቸው።
[25]በልባቸው፣ "እሰይ! ያሰብነው ተሳካ!
ዋጥ አደረግነውም" አይበሉ።
[26]በጭንቀቴ ደስ የሚላቸው፣

35፥3 ዘኍ25፥7፤ ኢሱ8፥18፤መዝ27፥1
35፥4 መዝ25፥3፤ 38፥12፤40፥14፤69፥6፡ 19፤70፥2፤83፥17፤129፥5፤ኢሳ45፥16፤ኤር4፥30፤ሚል2፥9
35፥5 ኢዮ13፥25፤ መዝ1፥4፤34፥7
35፥7 ኢዮ9፥31፤ 18፥8፤መዝ7፥4፡15፤55፥23
35፥8 መዝ7፥15፤ ኢሳ47፥11፤1ተሰ5፥3
35፥9 መዝ2፥11፤ 9፥14፤13፥5፤27፥1፤ ሉቃ1፥47
35፥10 ዘፀ9፥14፤ መዝ12፥5፤18፥17፡31፤37፥14፤74፥21፤86፥1፤109፥16፤113፥5፤140፥12፤ኢሳ41፥17
35፥11 ዘፀ23፥1፤ ማቴ26፥60
35፥12 መዝ38፥20፤ 109፥5፤ምሳ17፥13፤ኤር18፥20
35፥13 2ሳሙ3፥31፤1ነገ20፥31፤ኢዮ30፥25፤መዝ30፥11፤69፥10፡11፤109፥24
35፥14 መዝ38፥6፤ 42፥9፤43፥2
35፥15 ኢዮ16፥10፤ 31፥29
35፥16 ኢዮ16፥9፤ መዝ22፥7፤ማር9፥18፤10፥34፤ሐሥ7፥54
35፥17 መዝ6፥3፤ 22፥20፤22፥21፤57፥4፤58፥6
35፥18 መዝ22፥22፡25፤42፥4፤109፥30
35፥19 ቍ7፤መዝ9፥13፤38፥19፤69፥4፤ ምሳ6፥13፤10፥10፤ ዮሐ15፥25
35፥20 መዝ38፥12፤55፥21፤ኤር9፥8፤ ሚክ6፥12
35፥21 ኢዮ16፥10፤ መዝ40፥15፤70፥3፤ ሕዝ25፥3
35፥22 ዘፀ3፥7፤ መዝ10፥1፡14 35፥23 1ሳሙ24፥15፤መዝ7፥6፤17፥13፤80፥2
35፥24 መዝ22፥17 35፥25 ቍ21፤መዝ124፥3፤ምሳ1፥12፤ሰቆ2፥16 35፥26 ኢዮ8፥22፤19፥5፤መዝ4፥1፤22፥17፤38፥16፤109፥29፤ ሚክ7፥10

[ɣ]16 ሰብዓ ሊቃናት እንዲሁ ሲሆን በዕብራይስጥ ግን ምናምንቴ ፌዘኞች ማለት ሊሆን ይችላል።

35፥3 *ነፍሴንም፤* የ6፥3 ማብ ይመ።

*35፥4-10፤* ጌታ የመዝሙረኛውን ጠላቶች እንዲሟገትና የእጃቸውንም እንዲከፍላቸው (የ5፥10 ማብ ይመ) የሚያሳስብ አቤቱታ ነው።

35፥4 *ለማጥፋት የሚያሤሩ፤* የ5፥9 ማብ ይመ።

35፥5-6 *የእግዚአብሔር መልአክ፤* 34፥7 እና ማብ ይመ።

35፥5 *እንዳለ እብቅ፤* የ1፥4 ማብ ይመ።

*35፥9-10፤* የ7፥17 ማብ ይመ።

35፥9 *ነፍሴ፤* የ6፥3 ማብ ይመ።

35፥10 *ድኻውን ... ችግረኛውን፤* 34፥6 እና ማብ ይመ።

*35፥11-18፤* በአዲስ መልክ የቀረበ አቤቱታ ሲሆን (ቍ 17) አቤቱታው ከተሰማለት ምስጋና የሚያቀርብ መሆኑን ቃል ይገባል (ቍ 18)፤ ፍቅሩንና ወዳጅነቱን ያሳያቸው ሰዎች ግን በመልካም ፈንታ ክፉ መልሰውለታል።

35፥12 *ነፍሴንም፤* የ6፥3 ማብ ይመ።

35፥13 *ማቅ፤* የሐዘን ምልክት ነው (30፥11፤ ዘፍ37፥34 ይመ)። *በጾም፤* ከልብ ንስሓ መግባትን ያሳያል (69፥10 ይመ)።

35፥15 *ስሰናከል፤* የተሰናከለው በምግባራዊ ጉዳዮች አይደለም፤ ሁኔታዎች ግን ክፉኛ ደቀሰውታል (9፥3፤27፥2፤ 37፥24፤ 56፥13፤ 119፥165 ይመ)።

35፥16 *ጥርሳቸውንም አፋጩብኝ፤* በመረረ ጥላቻ ተነሡብኝ ማለት ነው (37፥12፤ ሰቆ2፥16 ይመ)።

35፥17 *እስከ መቼ?* የ6፥3 ማብ ይመ (እንዲሁም በመግቢያው ላይ "ትምህርተ መለኮት" የሚለውን ይመ)። *ከአንበሶች፤* የ7፥12 ማብ ይመ።

35፥18 *ጉባኤ፤* የ1፥5 ማብ ይመ።

*35፥18-19፤* ፍርድ ይሰጥ ዘንድ በአዲስ መልክ የቀረበ አቤቱታ ሲሆን፣ ነገሩን ከመጨረሱ በፊት ምስጋና ለማቅረብ ቃል ይገባል (ቍ 28)።

35፥19 *ከምድር ተነሥተው ጠላቶቼ የሆኑት፤* ቍ 11-17 ይመ። በዳዊት መዝሙር ውስጥ በተደጋጋሚ የሚንጸባረቅ ገጠመኝ ነው (38፥19፤ 69፥4፤109፥3፤ 119፥78፡86፡161 ይመ)፤ እንዲሁም ሰቆ 3፥52 ይመ። *እንዲያው የሚጠሉኝ፤* 69፥4 ይመ። በዮሐ 15፥25 ላይ የትኛው ክፍል እንደ ተጠቀሰ በእርግጠኝነት መናገር አይቻልም። ሁለቱም መዝሙሮች ግን ጌታ ኢየሱስ የነበረበትን ሁኔታ ያንጸባርቃሉ (የሆነ ሆኖ የመዝ69 መግቢያን ይመ)።

35፥21 *እሰይ! እሰይ!* ቍ 25፤ የ3፥2 ማብ ይመ።

35፥22 *ዝም አትበል፤* አይተህ እንዳላየህ ችላ አትበል ማለት ነው (28፥1 እና የ83፥1፤ የ109፥1 ማብ ይመ)።

35፥23 *ተነሥ፤* የ3፥7 ማብ ይመ። *ተንቀሳቀስ፤* የ7፥6 ማብ ይመ።

35፥24 *በጽድቅህ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

35፥25 *ዋጥ አደረግነውም፤* 124፥3 ይመ።

*35፥26፤* ለክፉ ሐሳባቸው የሚሰጠው ፍርድ ተመጣጣኝ እንዲሆን በድጋሚ የቀረበ ጥያቄ ነው (4-10 ይመ)።

ይፈሩ፤ ግራም ይጋቡ፤
በእኔ ላይ ራሳቸውን ከፍ ከፍ የሚያደርጉ፣
እፍረትንና ውርደትን ይከናነቡ።
[27]ፍትሕ ማግኘቴን የሚወዱ፣
እልል ይበሉ፤ ሐሤትም ያድርጉ፤
ዘወትርም፣ "የባርያው ሰላም ደስ የሚለው፣
*እግዚአብሔር* ከፍ ከፍ ይበል!" ይበሉ።
[28]አንደበቴ ጽድቅህን፣
ምስጋናህንም ቀኑን ሙሉ ይናገራል።

## መዝሙር 36

## የኀጥእ ክፋት፣ የእግዚአብሔር በጎነት

*ለመዘምራን አለቃ፤ የእግዚአብሔር ባሪያ የዳዊት መዝሙር*

[1]ክፉውን ሰው፣
በደል በልቡ ታናግረዋለች፤[f]
እግዚአብሔርን መፍራት፣
በፊቱ የለም፤
[2]በደሉ ግልጽ ወጥቶ እንዳይጠላ፣
ራሱን በራሱ እጅግ ይሸነግላልና።
[3]ከአንደበቱ የሚወጣው የክፋትና የተንኰል
ቃል ነው፤
ማስተዋልንና በጎ ማድረግን ትቶአል።
[4]በመኝታው ላይ ክፋትን ያውጠነጥናል፤
ራሱን በጎ ባልሆነ መንገድ ይመራል፤
ክፋትንም አያርቅም።
[5]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ምሕረትህ እስከ
ሰማያት ይደርሳል፤
ታማኝነትህም እስከ ጠፈር ይመጥቃል።
[6]ጽድቅህ እንደ ታላላቅ ተራሮች፣
ፍርድህም እጅግ ጥልቅ ነው፤
*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ ሰውንም
እንስሳንም ታድናለህ።
[7]አምላክ ሆይ፤ ምሕረትህ እንዴት ክቡር
ነው!
የሰዎች ልጆች ሁሉ፣
በክንፎችህ ጥላ ሥር መጠጊያ ያገኛሉ።
[8]ከቤትህ ሲሳይ ይመገባሉ፤
ከበረከትህም ወንዝ ይጠጣሉ።
[9]የሕይወት ምንጭ ከአንተ ዘንድ ነውና፤
በብርሃንህም ብርሃን እናያለን።

35፥26 ኢዮ8፥22፤ 19፥5፤መዝ4፥1፤22፥17፤38፥16፤109፥29፤ ሚክ7፥10
35፥27 ኢዮ17፥3፤ መዝ9፥4፤20፥5፤33፥3፤መዝ147፥11፤149፥4
35፥28 መዝ5፥8፤ 51፥14፤71፥15፡24፤72፥15
36፥1 ኢዮ21፥6፤ 23፥15፤ኤር2፥19፤36፥16፡24፤ሮሜ3፥18
36፥2 ዘዳ29፥19
36፥3 ኢዮ5፥13፤ መዝ5፥6፡9፤10፥7፤43፥1፤94፥8፤144፥8፡11፤ ኢሳ44፥20፤ኤር4፥22፤13፥23፤አሞ3፥10
36፥4 መዝ52፥3፤ ምሳ4፥16፤ኢሳ65፥2፤ ሮሜ12፥9
36፥5 መዝ57፥10፤ 71፥19፤89፥1፡2፤103፥11፤108፥4፤119፥90
36፥6 ዘፍ1፥2፤7፥11፤ነሀ9፥6፤መዝ5፥8፤ 68፥15፤104፥14፤ 145፥16
36፥7 ሩት2፥12፤ መዝ6፥4፤17፥8፤57፥1፤91፥4 36፥8 ኢዮ20፥17፤ መዝ23፥2፤63፥5፤65፥4፤ኢሳ25፥6፤ ኤር31፥12፡14፤ራእ22፥1 36፥9 መዝ4፥6፤ 27፥1፤76፥4፤87፥7፤ 104፥2፤ምሳ10፥11፤ 16፥22፤ኢሳ2፥5፤9፥2፤60፥1፡19፤ኤር2፥13፤ ዮሐ1፥4፤1ጴጥ 2፥9

[f] 1 *ወይም ... ኃጢአት ከኀጥእ ይመነጫል*

*35፥27፤* የእግዚአብሔር "አገልጋይ" (እዚህ ላይ "አገል ጋይ" ሲባል "የተቀባው" ማለት ነው፤ የ2፥2 ማብ ይመ) አጋር የሆኑ ሁሉ ጌታን የሚያመሰግኑበትና በእርሱም ደስ የሚሰኙበት በቂ ምክንያት አላቸው።

35፥28 *ጽድቅህን፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

*መዝሙር 36፤* መዝሙረኛው ስለ እምነተ ቢሶች ክፋትና ስለ እግዚአብሔር ቸርነት በሚያሰላስልበት ወቅት እግዚአብሔር በዘላለማዊ ፍቅሩ ጥበቃውን እንዲያበዛለት ያቀረበው ጸሎት ነው። ቍ7-10 በአይሁድ የሃይማኖት ሥርዐት ውስጥ ከንግሥ ጸሎት ውስጥ የሚመደብ ነው።

36ርእስ *ለመዘምራን አለቃ፤* የመዝ4 የርእስ ማብ ይመ። *የእግዚአብሔር ባሪያ፤* የመንግሥቱ አገልጋይ ማለት ነው (የመዝ 18 ርእስ እና የ35፥27 ማብ እንዲሁም 2ሳሙ7፥20 ይመ)።

*36፥1-4፤* የክፉዎችን ቂልነት፣ እምነተ ቢስነትና ትዕቢት የሚያመለክት ክፍል ነው።

36፥1 *ታናግረዋለች፤* ይህ ቃል ሁልጊዜ የተያያዘው እግዚአብሔር በነቢያቱ አፍ ከሚናገረው ቃል ጋር ነው (ለምሳሌ ዘኍ23፥7፤ ኢሳ 13፥1፤ ኤር23፥33-38፤ ሕዝ12፥10 እንዲሁም የዘኍ23፥7 ማብ ይመ)። በዚህ ቦታ ቃሉ የተዛመደው የክፉዎችን ባሕርይ ከሚያሳይ ሁኔታ ጋር ሲሆን ምናልባት በቅጽበት ብልጭ ያለ ነገር ሳይሆን አይቀርም። *ልቡ፤* የ4፥7 ማብ ይመ። *እግዚአብሔርን መፍራት ... የለም፤* 55፥19 ይመ፤ የእግዚአብሔር ዐይኖች ሁሉንም ነገር እንደሚመለከቱ፣ ፍርዱም ቅን እንደ ሆነና የእጃቸውንም ለመክፈል ብርቱና ኀያል እንደ ሆነ አያስተውሉም (የ10፥11 ማብ ይመ)። ሐዋርያው ጳውሎስ ይህንን ምንባብ እንዴት እንዳ ገናዘበው ሮሜ3፥18 ይመ።

36፥2 *በራሱ ይሸነግላል፤* ራሱን ከመጠን በላይ ከማግነኑ የተነሣ በኀጢአቱ እንደሚቀጣና ተጠያቂም እንደሚሆን አያስብም።

36፥3 *ከአንደበቱ የሚወጣው፤* የ5፥9 ማብ ይመ። *ማስተዋልን ... ትቶአል፤* 94፥8-11፤ ምሳ2፥9-11 ይመ። *በጎ ማድረግን፤* 34፥8-14 እና ማብ ይመ።

36፥4 *በመኝታው ላይ፤* ሐሳቡ ነጻ በሚሆንበትና በማግስቱ የሚሠራውን ነገር ሲያወጣ ሲያወርድ ማለት ነው፤ ክፉዎች የእግዚአብሔርን ሕግ ሟትና ማታ አያሰላስሉም (1፥2፤ 119፥55 ይመ)፤ ወይም እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው እንዲያስተምራቸው አያደርጉም (16፥7 ይመ)፤ ወይም በሌሊት ከእግዚአብሔር ጋር በጸሎት አይነጋገሩም (42፥8 ይመ)፤ ስለ እርሱም አያስቡም (63፥6)፣ ተስፋውንም አያሰላስሉም (119፥148 ይመ)። *ክፋትንም አያርቅም፤* ክፉዎች ኀጢአትን አይጠሉም፤ (1) ኀጢአትን መጥላት የእግዚአብሔር ባሕርይ ነው (ምሳ6፥16፤ ኤር 44፥4፤ ዕን 1፥13) ደግሞም የኢየሱስ ክርስቶስ አገልግሎት መሠረት ነው (45፥7)፤ (2) ሰዎች ሌሎችን የሚወዱ፣ ለሌሎች የሚያስቡና ድኾችንም የሚረዱ ሊሆኑ ይችላሉ፤ ሆኖም ከኀጢአት የማይርቁ፣ ከዓለም ክፉ ሐሳብ ጋር የማይተባበሩ፣ ለፍትህ የማይቆረቆሩ ወይም ክፉን የማይጠሉ ከሆነ በእግዚአብሔር ፊት ሊቆሙና መንፈስ ቅዱስንም ሊከተሉ አይችሉም (ከገላ5፥16-24 ጋር ያነጻጽሩ)። "እግዚአብሔርን የሚወዱ ክፋትን ይጥሉ" (97፥10)።

*36፥5-9፤* የእግዚአብሔር ቸርነት፣ ይኸውም ለፍጥረቱ ሁሉ የሚያደርገው በጎነት በዚህ ክፍል ተመልክቶአል (33፥4-5 ይመ)።

36፥5 *ምሕረትህ ... ታማኝነትህም፤* ፍቅርህና ታማኝነትህ ማለት ነው (ይኸውም በ57፥3፤ 61፥7፤ 85፥10፤ 86፥15፤ 89፥14፤ 115፥1፤ 138፥2፤ በምሳ3፥3፤ 14፥22፤ 16፥6፤ 20፥28 ላይ እንደ ተገለጠው ዐይነት ማለት ነው (የ3፥7 ማብ ይመ)። *እስከ ጠፈር ይመጥቃል፤* ፍጥረት ሁሉ በሚኖርበት ስፍራ ሰፍኖ ይገኛል ማለት ነው (57፥10፤ 108፥4 ይመ)።

36፥6 *ጽድቅህ ... ፍርድህም፤* ጽድቅህና ፍርድህ ማለት ነው (ይኸውም በ33፥5፤ 89፥14፤ 97፥2፤ በሆሴ2፥19 ላይ እንደ ተገለጠው ዐይነት ማለት ነው፤ እንዲሁም ኢሳ9፥7፤ 33፥5፤ ኤር 9፥24 ይመ)። *ጽድቅህ፤* የ4፥1 ማብ ይመ። *ታላላቅ ተራሮች ... ጥልቅ፤* ከፍታው እንደተራራ፣ ጥልቀቱም እንደ ባሕር የሆነ ማለት ነው።

36፥7 *ምሕረትህ፤* ቍ5፤ እንዲሁም የ6፥4 ማብ ይመ። *የሰው ልጆች ሁሉ፤* በማንኛውም የኑሮ ክልል ውስጥ የሚገኙ ሰዎች ማለት ነው። *በክንፎችህ ጥላ ሥር፤* 17፥8 እና ማብ ይመ።

36፥8 *ይመገባሉ ... ይጠጣሉ፤* ሕይወትን የሚሰጥ ምግብና መጠጥ ማለት ነው። *በቤትህ፤* በዚህ ቦታ ይህ አባባል የሚያመለክተው እግዚአብሔር ለሕያዋን ፍጥረታት ሁሉ የሚሆን ምግብ ያከማቸበትን ቦታ ነው (24፥2 ይመ)። *ወንዝ፤* እግዚአብሔር ዝናብን ከላይኛው ማንዶልዶያ "ከግምጃ ቤቱ" (ከዕቃ ቤቱ) የሚያወርድበት ነው (33፥7፤ ኢዮ38፥8-11፡22፡37፤ ኤር 10፥13 ይመ)፤ ይህ ግልጽ ምስላዊ አነጋገር እግዚአብሔር ከሰማይ የሚፈልቀውን ውሃና በሚፈስበት አቅጣጫ ሁሉ የምድር ወንዞችንና ምንጮችን እየመገበ ሕይወትንና ሰላምን የሚሰጠውን ውሃ የሚቆጣጠር መሆኑን ያሳያል፤ ይህ ውሃ ከእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ለሚወጣው "የሕይወት ውሃ ወንዝ" ምንጭ ምልክት ነው (ራእ22፥1 እንዲሁም ሕዝ47፥1-12 ይመ)። *ከበረከትህም፤* አያሌ የደስታ ምንጭ ከሚያስገኝልን ማለት ነው።

*36፥9፤* በቍ5-9 ያለውን ሐሳብ የሚያጠቃልልና ከፍጻሜው ላይ የሚያደርስ ነው። *የሕይወት ምንጭ፤* ኤር2፥13፤ 17፥13 ይመ። በመጨረሻ እግዚአብሔር በክርስቶስ አማካይነት ለኀጢአተኞች የሕይወትን ውሃ አዘጋጀ (ዮሐ4፥10፡14)። *በብርሃንህ፤* 27፥1 እና ማብ ይመ። *እናያለን፤* እውን ሆኖ እንመለከታለን፤ እናገኛለን፤ ደስታንም እንመለከታለን ማለት ነው፤ ይኸውም

[10]ለሚያውቁህ ምሕረትህ፣
ልባቸውም ለቀና ጽድቅህ ዘወትር
አይቋረጥባቸው::
[11]የትዕቢተኛ እግር በላዬ አይምጣ፤
የክፉውም ሰው እጅ አያሳደኝ::
[12]ክፉ አድራጊዎች እንዴት እንደ ወደቁና
እንደ ተጋደሙ፣
ቍልቍልም እንደ ተወረወሩና መነሣት
እንደማይችሉ ተመልከት!

## መዝሙር 37[a]

### የጻድቁና የክፉው ዕጣ ፈንታ

የዳዊት መዝሙር

[1]ዐመፀኞችን በማየት አትሸበር፤
በክፉ አድራጊዎችም አትቅና፤
[2]እንደ ሣር ፈጥነው ይደርቃሉና፤
እንደ ለምለም ቅጠልም ይጠወልጋሉ::
[3]*በእግዚአብሔር ታመን፤* መልካምንም
አድርግ፤
በምድሪቱ ተቀመጥ፤ ዘና ብለህ ተሰማራ::
[4]*በእግዚአብሔር* ደስ ይበልህ፤
የልብህንም መሻት ይሰጥሃል::
[5]*መንገድህን ለእግዚአብሔር* ዐደራ ስጥ፤
በእርሱ ታመን፤ እርሱም ያከናውንልሃል፤
[6]ጽድቅህን እንደ ብርሃን፣
ያንተን ፍትሕ እንደ ቀትር ፀሓይ
ያበራዋል::
[7]*በእግዚአብሔር ፊት* ጸጥ በል፤
በትዕግሥትም ተጠባበቀው፤
መንገዱ በተቃናለት፣
ክፋትንም በሚሸርብ ሰው ልብህ
አይሸበር::
[8]ከንዴት ተቈጠብ፤ ቍጣንም ተወው፤
ወደ እኵይ ተግባር እንዳይመራህ
አትከፋ::
[9]ክፉ ሰዎች ይጠፋሉና፤
*እግዚአብሔርን* ተስፋ የሚያደርጉ ግን
ምድርን ይወርሳሉ::

36፥10 መዝ7፥10፤ 11፥2፤94፥15፤125፥4 ፤ኤር9፥24፤22፥16፤ 31፥3
36፥11 መዝ71፥4፤ 140፥4
36፥12 መዝ18፥38
37፥1 መዝ73፥3፤ ምሳ3፥31፤23፥17-18፤24፥19
37፥2 ቍ38፤2ነገ 19፥26፤ኢዮ14፥2፤ መዝ90፥6፤92፥7፤102 ፥4፤ኢሳ40፥7፤ያዕ 1፥10
37፥3 ዘዳ30፥20፤ ሕዝ34፥14፤ዮሐ10፥9
37፥4 ኢዮ7፥6፤ 27፥10፤መዝ21፥2፤14 5፥19፤ማቴ6፥33
37፥5 መዝ4፥5
37፥6 ኢዮ11፥17 ፤መዝ18፥24፤103፥17 ፤112፥3
37፥7 ቍ1፤ ዘፀ14፥ 14፤መዝ21፥11፤26፥ 10፤27፥14፤40፥1፤ 119፥150፤130፥5፤ ኢሳ38፥13፤41፥1፤ ኤር 12፥1፤ዕን3፥16፤ ሮሜ8፥25
37፥8 ቍ1፤ኤፌ 4፥31፤ቈላ3፥8
37፥9 ቍ22፤መዝ 25፥13፤31፥22፤101፥8፤118፥10፤ምሳ2፥22፤ኢሳ 25፥9፤26፥8፤40፥ 31፤49፥8፡23፤51፥5፤57፥13፤ ማቴ5፥5

[a] ም37 የዚህ መዝሙር እያንዳንዱ ጥቅስ ተከታታይ ፊደላት ባሉት የዕብራይስጥ ሆሄያት የሚጀምር ሲሆን ጅማሬው ወይም ጅማሬውና መጨረሻው ትርጕም የሚሰጥ ግጥም ነው::

በ16፥10፤ 27፥13፤ 34፥8፡12፤49፥9፡19፤ 89፥48፤ 90፥15፤ 106፥5 ላይ እንደ ተመለከተው እንዲሁም ("ደስ ይለን ዘንድ") ኢዮ9፥25 ("በጨረፍታ አያይም") 42፥2፤ ማሕ1፥16 ("ጨመርሁ") 3፥13 ("ይለው ዘንድ") 6፥6 ("መልካምን ቢያዩ") 8፥16፤ ኢሳ53፥10፤ ሰቆ3፥1:: *ብርሃን፤* ከመጀመሪያም ሲፈጠር የተትረፈረፈ እንዲሆን ነው:: ብርሃን፣ ከሕይወት ጋር ያለውን ትስስር ለማስተዋል 49፥19፤ 56፥13፤ ኢዮ3፥20፤ 33፥30፤ ኢሳ53፥11 ይመ::

*36፥10-11፤* ጸሎት ነው፤ በፍጥረትህ ሁሉ ላይ ያሳየኸው "ፍቅርህ" (ቍ5) እና "ጽድቅህ" (ቍ6) ለሚገዙልህና በቅንነትም በፊት ለሚመላለሱ ሁሉ ግልጽ ሆኖ ይታያል፤ ክፉዎች ግን በእኔ ላይ እንዳይነሱ "እግራቸውንና እጃቸውን" አስርልኝ ማለት ነው (*ንጉሡ፤* የ33፥16 ማብ ይመ)::

36፥10 *ምሕረትህ፤* የ6፥4 ማብ ይመ:: *ጽድቅህ፤* የ4፥1 ማብ ይመ::

36፥11 *የትዕቢተኛ፤* የ31፥23 ማብ ይመ::

*36፥12፤* ልበ ሙሉነትን ያመለክታል (የ3፥8 ማብ ይመ):: *መነሣትም እንደማይችሉ፤* ሞት አሸንፎት ሊሆን ይችላል (የ13፥4 ማብ ይመ)::

*መዝሙር 37፤* እግዚአብሔርን መፍራት ጥበብ መሆኑን የሚያስገነዝብ ትምህርት ነው፤ ("የጥበብ መዝሙር" በመባል የሚታወቁ ሌሎች መዝሙሮች እንዳሉ በ34፥8-22፤ 49፤ 112 ላይ ይመ፤ ከዚህ መዝሙር ጋር የጠበቀ ትስስር ያላቸው ሌሎች መዝሙሮችም የሚከተሉት ናቸው፤ መዝ73፤91፤92፥6-9፡12-15፤ 111፤119፤127-128፤133፤ በመጽሐፈ ምሳሌ መግቢያ ላይ "የጥበብ መጻሕፍት" የሚለውን ይመ):: የዚህ መዝሙር ዐቢይ ሐሳብ በመዝሙር 36 ላይ በክፉዎችና በጻድቃን መካከል ተነጻጽሮ ከቀረበው ሐሳብ ጋር በብዙ ይዛመዳል:: በመዝሙሩ ላይ ገኖ የምናገኘው ሐሳብ "ምድሪቱን የሚወርስ" ማን ነው (ቍ9፡11፡22፡29)? የሚለው ነው፤ በሌላ አነጋገር በተስፋዪቱ ምድር የእግዚአብሔርን በረከት የሚያገኝ ማን ነው? የሚል ነው:: የተስፋዪቱን ምድር የሚወርሱት ሌሎችን የሚያውጠነጥኑ (ቍ12)፣ ነገር የሚሸርቡ (ቍ7፡32)፣ የተበደሩትን የማይከፍሉ (ቍ21)፣ ጥቅምን ለማግኘት የሚያደቡና (ቍ14) ከዚህም የተነሣ ነገር ሁሉ የተከናወነላቸው መስለው የሚታዩ ክፉዎች ናቸውን (ቍ7፡16፡35)? ወይስ በጌታ የሚታመኑ (ቍ3፡5፡7፡34)፣ ከዚህም የተነሣ ገሮች (ቍ11)፣ ነቀፋ የሌለባቸው (ቍ18፡37)፣ ለጋሶች (ቍ21፡26)፣ ትክክለኞች (ቍ37)፣ ሰላም ወዳዶች (ቍ37)፣ ከአንደበታቸው የሚወጣው ቃል በልባቸው የሚያሰላስሉትን የእግዚአብሔርን ሕግ የሚያንጸባርቅ ጻድቃን (ቍ30-31)? የክፉዎች ባሕርይ ምን እንደሚመስል ለማየት 10፥2-11፤ 73፥4-12 ይመ:: እንዲሁም የጻድቃን ባሕርይ ምን እንደሚመስል ለማየት መዝ112 ይመ:: የክፉዎች ዘመን አጭር መሆኑን ለማየት መዝ49፤ 73፥18-20 ይመ:: የዚህ መዝሙር ዐቢይ ሐሳብ አድጎ የሚታየው በቍ1-11 ላይ ሲሆን በደበልጥ ደግሞ ቀጥሎ ባሉት ቍጥሮች ላይ የመዝሙሩ ዐቢይ ሐሳብ በሰፊው አድጎ ይታያል:: የመዝሙሩ ጠቅላላ ሐሳብ የተቀነበበው የክፉዎች ዘመን አጭር መሆኑን በሚያመለክተው ሐሳብና (ቍ1-2) ጌታ ግን ጻድቃንን እስከ መጨረሻው አቅፎና ደግፎ እንደሚይዛቸው በሚያመለክተው ሐሳብ ነው (ቍ39-40)::

*37፥1-2፤* ቍ7፤ መዝ 73 ይመ::

*37፥2፤* የቍ20 ማብ ይመ::

*37፥3፤* 34፥8-14 እና ማብ ይመ::

37፥4 *በእግዚአብሔር ደስ ይበልህ፤* በጌታ ደስ ይበላችሁ ሲባል የጌታን ባጠገባችሁ መሆንና የቃሉንም እውነትና ጽድቅ ባጠገባችሁ መሆን ከልብ ናፍቁ ማለት ነው (ከኢዮ 22፥26፤ 27፥10፤ ከኢሳ58፥14 ጋር ያነጻጽሩ):: በጌታ ደስ ለሚሰኙት፣ እግዚአብሔር የልባቸውን መሻት ይሰጣቸዋል፤ (1) ፍላጎታችንና ጥያቄአችን እንደ ፈቃዱ ከሆነ እግዚአብሔር ከልብ የጠየቅነውን ነገር ሁሉ ይመልስልናል (ዮሐ15፥7 ይመ):: (2) በእግዚአብሔርና በፈቃዱም ደስ የሚለን ከሆነ፣ እግዚአብሔር ራሱ የራሱን ሐሳብ በልባችን ውስጥ ያስቀምጣል (ፊል2፥13 ይመ)::

37፥5 *ዐደራ ስጥ፤* 1ጴጥ5፥7 ይመ::

37፥6 *ጽድቅህን እንደ ብርሃን ... ያበራዋል፤* በኀጢአት ምክንያት በደል የደረሰባቸው ጻድቃን፣ ከዚህ የሚከተሉትን በጎ ነገሮች እንደሚያገኙ ተስፋ ተገብቶላቸዋል፤ (1) ለጸሎታቸው መልስ ያገኛሉ (ቍ4-5)፤ (2) የጽድቅ መንገዳቸው ይባረክላቸዋል (ቍ6) (3) ሰማያዊ ርስትን ያገኛሉ (ቍ9፡11፡34)፤ (4) የጌታ እርዳታ ዘወትር ከእነርሱ ጋር ይሆናል (ቍ17-19፡39)፤ (5) የጌታ ምሪትና ጥበቃም ከእነርሱ ጋር ይሆናል (ቍ23-25፡28)፤ (6) ድነትም የእነርሱ ነው (ቍ6)::

37፥7 *በትዕግሥትም ተጠባበቀው፤* ይህ መዝሙር ክፉዎች በመንገዳቸው ሁሉ ኀጢአተኛና ጠማማ ሆነው ሳለ ቢበለጽጉና ነገርም ሁሉ ቢሳካላቸው ጻድቃን ይህንን ሁኔታ እንዴት መመልከት እንዳለባቸው ማሳሰቢያ ይሰጣል፤ እግዚአብሔር ቅን ፍርዱን እስኪያሳይና ነጻም እስኪያወጣን ድረስ በእምነት መጽናት ይኖርብናል (ከቍ1፥73፤ ከምሳ3፥31፤ 23፥17፤ 24፥1፤ ከኤር12 ጋር ያነጻጽሩ):: በችግርና በሥቃይ ውስጥ ጸንቶ ማለፍ የሚቻለው መንፈስ ቅዱስ ሲረዳንና ሲያግዘን ብቻ ነው (ገላ5፥22፤ ሮሜ8፥3-4 ይመ፤ ከኤፌ4፥1-2፤ ከቈላ1፥11፤3፥12 ጋር ያነጻጽሩ)፤ መንፈስ ቅዱስ፣ እግዚአብሔር ክፉዎችን እንደሚቀጣና ለእኛም ሽልማትን እንደሚያዘጋጅ አስቀድሞ አረጋግጦልናል (ከሮሜ 8፥28፤ ከዕብ12፥1-2፡5-13 ጋር ያነጻጽሩ)::

37፥8 *ከንዴት ... ቍጣንም፤* በጻድቃን ላይ እየተረማመዱ ያግበሰበሱት ሀብት ዋስትና እንደሌለው አንዱ ማስረጃ ነው::

37፥9 *ምድርን ይወርሳሉ፤* ከእግዚአብሔር ዋስትና ያለውን የርስት መያዣ (እነርሱና ልጆቻቸው) ይቀበላሉ፤ ይህች ምድር ለእግዚአብሔር ሕዝቦች መኖሪያ ትሆን ዘንድ የተበጀችና የተቤ

10 ለአፍታ እንጂ፣ ክፉ ሰው አይዘልቅም፤
 ስፍራውንም ብታስስ አታገኘውም።
11 ገሮች ግን ምድርን ይወርሳሉ፤
 በታላቅ ሰላምም ሐሤት ያደርጋሉ።

12 ክፉዎች በጻድቃን ላይ ያሤራሉ፤
 ጥርሳቸውንም ያፋጩባቸዋል።
13 እግዚአብሔር ግን ይሥቅባቸዋል፤
 ቀናቸው እንደ ደረሰ ያውቃልና።

14 ድኾችንና ችግረኞችን ለመጣል፣
 አካሄዳቸው ቀና የሆነውንም ለመግደል፣
ክፉዎች ሰይፋቸውን መዘዙ፤
 ቀስታቸውንም ገተሩ።
15 ሰይፋቸው የገዛ ልባቸውን ይወጋል፤
 ቀስታቸውም ይሰበራል።

16 የጻድቅ ጥቂት ሀብት፣
 ከክፉዎች ብዙ ጥሪት ይበልጣል።
17 የክፉዎች ክንድ ይሰበራልና፤
 ጻድቃንን ግን እግዚአብሔር ደግፎ
 ይይዛቸዋል።

18 *እግዚአብሔር* የንጹሓንን የሕይወት
 ዘመን ያውቃል፤
 ርስታቸውም ለዘላለም ይኖራል።
19 በክፉ ጊዜ ዐንገት አይደፉም፤
 በራብ ዘመንም ይጠግባሉ።
20 ክፉዎች ግን ይጠፋሉ፤
 የ*እግዚአብሔር* ጠላቶች እንደ መስክ
 ውበት ይሆናሉ፤
 ይጠፋሉ፤ እንደ ጢስም ተነው ይጠፋሉ።

21 ኀጢአተኛ ይበደራል፤ መልሶም
 አይከፍልም፤
 ጻድቅ ግን ይቸራል።
22 *እግዚአብሔር* የባረካቸው ምድርን
 ይወርሳሉ፤
 እርሱ የሚረግማቸው ግን ይጠፋሉ።

23 የሰው አካሄድ በ*እግዚአብሔር* ይጸናል፤
 በመንገዱ ደስ ይለዋል።
24 ቢሰናከልም አይወድቅም፤
 *እግዚአብሔር* በእጁ ደግፎ ይይዘዋልና።

25 ጕልማሳ ነበርሁ፤ አሁን አርጅቻለሁ፤
 ነገር ግን ጻድቅ ሲጣል፣
 ዘሩም እንጀራ ሲለምን አላየሁም።
26 ሁልጊዜ ቸር ነው፤ ያበድራልም፤
 ልጆቹም የተባረኩ ይሆናሉ።

27 ከክፉ ራቅ፤ መልካሙንም አድርግ፤
 ለዘላለምም ትኖራለህ።
28 *እግዚአብሔር* ፍትሕን ይወዳልና፤
 ታማኞቹንም አይጥልም፤

ለዘላለምም ይጠብቃቸዋል፤
 የኀጢአተኛው ዘር ግን ይጠፋል።
29 ጻድቃን ምድርን ይወርሳሉ፤
 በእርሷም ለዘላለም ይኖራሉ።

30 የጻድቅ አፍ ጥበብን ይናገራል፤
 አንደበቱም ፍትሐዊ ነገር ያወራል።
31 የአምላኩ ሕግ በልቡ አለ፤
 አካሄዱም አይወላገድም።

32 ክፉዎች ጻድቁን ይከታተሉታል፤
 ሊገድሉትም ይሻሉ።
33 *እግዚአብሔር* ግን በእጃቸው
 አይጥለውም፤
 ፍርድ ፊት ሲቀርብም አሳልፎ
 አይሰጠውም።
34 *እግዚአብሔርን* ደጅ ጥና፤
 መንገዱንም ጠብቅ፤
ምድሪቱን ትወርስ ዘንድ ከፍ ከፍ
 ያደርግሃል፤
 ክፉዎችም ሲጠፉ ታያለህ።

37፥10 ኢዮ7፥10፤ ሕዝ27፥36
37፥11 ዘሌ26፥6፤ ዘኍ6፥26፤14፥24፤ ማቴ5፥5
37፥12 ኢዮ16፥9፤ መዝ2፥1፤31፥12፤ 35፥16፤112፥10
37፥13 1ሳሙ26፥10፤ሕዝ12፥23
37፥14 መዝ11፥2፤ 22፥20፤35፥10
37፥15 1ሳሙ2፥4፤ መዝ9፥16፤46፥9፤ኤር 49፥35
37፥16 ምሳ15፥16፤ 16፥8
37፥17 ኢዮ38፥15፤ መዝ10፥15፤41፥12፤1 40፥12፤145፥14፤ 146፥7
37፥18 ቍ27:29፤ ኢዮ23፥10፤መዝ 44፥21
37፥20 መዝ34፥21 ፤68፥2፤102፥3፤ኢሳ 51፥6
37፥21 ዘሌ25፥35፤ መዝ112፥5
37፥22 ቍ9፤ኢዮ 5፥3
37፥23 ዘኍ14፥8፤ ኢዮ11፥15፤መዝ 7፥9፤66፥9፤147፥11
37፥24 2ዜና9፥8፤ መዝ 13፥4፤27፥2፤ 38፥17፤41፥12፤55፥2 2፤119፥165፤145፥14 ፤ምሳ3፥23፤10፥9
37፥25 ቍ28፤ዘፍ 51፥11፤መዝ111፥5፤14 5፥15፤ማር10፥46፤ዕብ 13፥5
37፥26 ዘሌ25፥35፤ ዘዳ28፥4፤መዝ112፥2
37፥27 ዘኍ24፥21 ፤መዝ34፥14፤3ዮሐ 1፥11
37፥28 ዘፍ17፥14፤ ዘዳ7፥6፤32፥26፤መዝ 18፥25፤97፥10፤ምሳ2፥22 37፥29 ቍ9፤ምሳ 2፥21፤ኢሳ34፥17
37፥30 መዝ49፥3፤ ምሳ10፥13 37፥31 ዘዳ6፥6፤ 32፥35፤ኢዮ 22፥22 37፥32 መዝ10፥8፤ 11፥5 37፥33 ኢዮ32፥3፤ መዝ 34፥22፤79፥11፤2ጴጥ2፥9 37፥34 ቍ9፤መዝ18፥21፤27፥14፤52፥6

---

ዦች፣ የተትረፈረፈም ሀብት ምንጭ እንድትሆን የተደረገች ናት። በጌታ ተስፋ የሚያደርጉ ማለትም ሕይወትንና በረከትን የሚሰጥ ጌታ መሆኑን በጽኑ የሚያምኑ የተስፋዪቱን ምድር ይወርሳሉ፤ ከእግዚአብሔር ተለይተውና ክፉ መንገዳቸውንም ተጠቅመው ምድሪቷን ለመውረስና ሀብቷንም ለመብላት ደፋ ቀና የሚሉ ግን አያገኟትም (ቍ11:22:29 ይመ፤ ከያዕ7 ጋር ያነጻጽሩ)።

37፥10 *ለአፍታ፤* በዚህ ቦታ የጊዜው አጭርነት የሚያሳየው ሊመጣ ያለው ሁኔታ አይቀሬ መሆኑን ነው (58፥9፤ ኢዮ 20፥5-11፤ ሐጌ2፥6 ይመ)።

*37፥11፤* ማቴ5፥5 ይመ። *ገሮች፤* በእግዚአብሔር ቸርነትና ጸጋ የሚተማመኑ እንዲሁም ወንድሞቻቸውን ያልገፉ ማለት ነው፤ *በታላቅ ሰላም፤* ያልተቀየጠ በረከት ማለት ነው።

37፥12 *በጻድቃን፤* የ1፥5 ማብ ይመ። *ጥርሳቸውንም ያፋጩባቸዋል፤* 35፥16 እና ማብ ይመ።

37፥13 *እግዚአብሔር ግን ይሥቅባቸዋል፤* 2፥4 ይመ። *ቀናቸው እንደ ደረሰ ያውቃልና፤* በጣም የሚገርመው መዝሙረኛው በቍ22 ላይ ነገሩን በመጠኑ ያወሣው ቢሆንም እግዚአብሔር ክፉዎችን ድምጥማጣቸውን ለማጥፋት ከቶ የማይተኛ መሆኑን በቀጥታ የገለጸበት ሁኔታ የለም፤ የክፉዎች ሕይወት በእርግጥ "የሚጠፉ" መሆኑን በተመለከተ በተደጋጋሚ ተነግሮአል (ቍ9:22:28:34:38፤ ከቍ2:8:10:15:17:20:36:38 ጋር ያነጻጽሩ)፤ የክፉዎች ሕይወት አጭር እንደ ሆነ ጌታ ያውቃል፤ ለጻድቃን ግን ጥበቃውንና እንክብካቤውን ያበዛላቸዋል። *ቀናቸው፤* በ1ሳሙ26፥10 ላይ እንደ ተገለጸው ሁሉ ይህ አባባል ክፉዎች "የሚጠፉበትን" ዕለት ያመለክታል ("ጊዜው" በቀጥታ ሲተረጐም "ቀኑ" እንደ ማለት ነው)፤ ኢዮ18፥20 ("ዕጣ ፋንታው")።

37፥14 *ድኾችንና ችግረኞችን፤* 34፥6 እና ማብ ይመ።

37፥15 *ልባቸውን ይወጋል፤* 45፥5 ይመ።

37፥16-17 *ጻድቃን፤* የ1፥5 ማብ ይመ።

37፥18 *ንጹሓን፤* ቍ37፤ 15፥2፤ እንዲሁም የ26፥1 ማብ ይመ።

37፥20 *ውበት፤* ሣሩና አበባው ነው (ከቍ2፤ 90፥5-6፤ 102፥11፤ 103፥5-16፤ ከኢዮ14፥2፤ ከኢሳ40፥6-8 ጋር ያነጻጽሩ፤ ያዕ 1፥10-11 ይመ)።

*37፥21፤* "ክፉዎች ይበደሩ ዘንድ ግድ ነው፤ ዕዳቸውን መክፈል ግን አይችሉም፤ ጻድቃን ግን በልግስና መስጠት ይችላሉ" (ዘዳ15፥6፤ 28፥12:44 ይመ)።

*37፥24፤* ምሳ24፥16 ይመ።

*37፥26፤* የቍ21 ማብ ይመ።

37፥28 *ታማኞቹንም፤* የ4፥3 ማብ ይመ።

37፥29 *ለዘላለም፤* ከክፉዎች በተቃራኒው (ቍ28)፣ ጻድቃንና ልጆቻቸው፣ የልጅ ልጆቻቸውም ቃል በተገባላቸው ምድር ለዘላለም እንደሚኖሩ ያመለክታል።

37፥30 *ጥበብን፤* 119፥98:130፤ ዘዳ4፥6 ይመ።

37፥31 *በልቡ፤* የ4፥7 ማብ ይመ። *አይወላገድም፤* ቀና ከሆነው ጎዳና ማለት ነው (17፥5 ይመ)።

37፥32 *ይከታተሉታል፤* 10፥8-9፤ እንዲሁም የ7፥2 ማብ ይመ። *ሊገድሉትም ይሻሉ፤* የሐሰት ክስ በማቅረብ (ቍ33) ሕይወታቸውን ለማጥፋት ይሯሯጣሉ።

[35]ክፉና ጨካኙን ሰው፣
 እንደ ሊባኖስ ዝግባ ለምልሞ አየሁት፤
[36]ዳግመኛ በዚያ ሳልፍ፣ እነሆ፣ በቦታው
 አልነበረም፤
 ብፈልገውም አልተገኘም።
[37]ንጹሐንን ልብ በል፤ ቅኑንም አስተውል፤
 የሰላም ሰው ተስፋ አለውና።[#]
[38]ኀጢአተኞች ግን በአንድነት ይጠፋሉ፤
 የክፉዎችም ዘር[1] ይወገዳል።
[39]የጻድቃን ድነት ከእግዚአብሔር ዘንድ
 ነው፤
 በመከራ ጊዜም መጠጊያቸው እርሱ
 ነው።
[40]እግዚአብሔር ይረዳቸዋል፤
 ይታደጋቸዋልም፤
 ከክፉዎች እጅ ነጥቆ ያወጣቸዋል፤
 እርሱን መጠጊያ አድርገዋልና
 ያድናቸዋል።

## መዝሙር 38

### የጭንቅ ሰዓት ጸሎት

የዳዊት መዝሙር፤ ለመታሰቢያ

[1]እግዚአብሔር ሆይ፤ በቍጣህ አትገሥጸኝ፤
 በመዓትህም አትቅጣኝ።
[2]ፍላጻዎችህ ወግተውኛልና፤
 እጅህም ተጭናኛለች።
[3]ከቍጣህ የተነሣ ሰውነቴ ጤና አጥቶአል፤
 ከኀጢአቴም የተነሣ ዐጥንቶቼ ሰላም
 የላቸውም።
[4]በደሌ ውጦኛል፤
 እንደ ከባድ ሸክምም ተጭኖኛል።
[5]ከንዝህላልነቴ የተነሣ፣
 ቍስሌ ሸተተ፤ መገለም፤
[6]ዐንገቴን ደፋሁ፤ ጐበጥሁም፤
 ቀኑንም ሙሉ በትካዜ ተመላለስሁ።
[7]ወገቤ እንደ እሳት ነደደ፤
 ሰውነቴም ጤና የለውም።
[8]እጅግ ዝያለሁ፤ ፈጽሞም ደቅቄአለሁ፤
 ከልቤም መታወክ የተነሣ እጮኻለሁ።
[9]ጌታ ሆይ፤ ምኞቴ ሁሉ በፊትህ
 ግልጽ ነው፤
 ጭንቀቴም ከአንተ የተሰወረ አይደለም።
[10]ልቤ በኀይል ይመታል፤ ጒልበት
 ከድቶኛል፤
 የዐይኔም ብርሃን ጠፍቶአል።
[11]ከቍስሌ የተነሣ ወዳጆቼም ባልንጀሮቼም
 ሸሹኝ፤
 ጎረቤቶቼም ርቀው ቆሙ።
[12]ሕይወቴን ለማጥፋት የሚሹ ወጥመድ
 ዘረጉብኝ፤
 ሊጐዱኝ የሚፈልጉ ሊያጠፉኝ ዛቱ፤
 ቀኑንም ሙሉ ተንኰል ይሸርባሉ።
[13]እኔ ግን እንደማይሰማ ደንቈሮ፣
 አፉንም መክፈት እንደማይችል ዲዳ
 ሆንሁ።
[14]በእርግጥም ጆሮው እንደማይሰማ፣
 አንደበቱም መልስ መስጠት እንደ
 ማይችል ሰው ሆንሁ።
[15]እግዚአብሔር ሆይ፤ በተስፋ
 እጠብቅሃለሁ፤
 ጌታ አምላኬ ሆይ፤ አንተ መልስ
 ትሰጠኛለህ።
[16]እኔ፣ "ጠላቶቼ በእኔ ላይ ደስ
 አይበላቸው፤
 እግሬም ሲንሸራተት፣ በላዬ
 አይኵራሩብኝ" ብያለሁና።

37፥35 ኢዮ5፥3
37፥36 ቍ10፤ምሳ 12፥7፤ኢሳ41፥12፤ዳን 11፥9
37፥37 ቍ18፤ዘፍ 6፥9፤መዝ11፥7፤18፥2 5፤ኢሳ57፥1-2
37፥38 ቍ2፡9፤መዝ 1፥1፤73፥19
37፥39 መዝ3፥8፤ 9፥9
37፥40 1ዜና5፥20፤ መዝ2፥12፤18፥48፤ 20፥2፤34፥7
38፥1 መዝ6፥1
38፥2 ኢዮ6፥4
38፥3 ኢዮ33፥19፤ ምሳ3፥8፤ኢሳ4፥22፤ 66፥14
38፥4 ዘኍ11፥14፤ ዕዝ9፥6፤መዝ40፥12 ፤65፥3፤ሉቃ11፥46
38፥5 ቍ11፤ኢዮ 19፥17፤መዝ69፥5፤14 7፥3፤ምሳ5፥23፤12፥2 3፤13፥16፤መክ10፥3
38፥6 መዝ35፥14፤ 57፥6፤145፥14፤146፥8
38፥7 ቍ3፤ኢዮ 14፥22
38፥8 መዝ6፥3፡6፤ 22፥1፤34፥18፤ምሳ 5፥11፤17፥22
38፥9 ኢዮ3፥24፤ መዝ119፥20፤143፥7
38፥10 ኢዮ37፥1፤ መዝ6፥7፤19፥8፤31፥ 10፤88፥9
38፥11 ቍ5
38፥12 መዝ31፥4፤ 35፥4፡20፤41፥5፤ 140፥5፤141፥9
38፥13 መዝ115፥6 ፤135፥17፤ኢሳ43፥8፤ ማር7፥37
38፥15 መዝ17፥6፤ 27፥14
38፥16 ዘዳ32፥35፤ መዝ22፥17

[#]37 ወይም *ዘር ይወጣለታል* [1]38 ወይም *ትውልድ*

*37፥35-36፤* ከቍ25-26 ጋር ያነጻጽሩ።

37፥37 *ንጹሐንን፤* የቍ18 ማብ ይመ።

*37፥37-39፤* አንዱ ተስፋ ያለው ሲሆን፣ ሌላው ተስፋ ቢስ መሆኑን የሚያሳይ ታላቅ ንጽጽር ነው።

37፥39-40 *የጻድቃን ... ይረዳቸዋል፤* ዕጣ ፈንታቸው በክፉዎች እጅ አይደለም፤ *መጠጊያቸው እርሱ ነው፤* ክፉዎች የሚያደርጉትን ቢያደርጉ ጌታ ግን ርስታቸውን ጠብቆ ያቈይላቸዋል።

*መዝሙር 38፤* ዳዊት በሠራው ኀጢአት እግዚአብሔር "ስለ ገሠጸውና" በዚህም ምክንያት ከባድ የሕመም ሥቃይ ስለ ደረሰበት ከዚህ ሁሉ ሥቃይ በፍጥነት ይገላግል ዘንድ ያቀረበው ልመና ነው። ይህ መዝሙር መቼ እንደ ተደረሰና በመዝሙረኛውም ላይ የደረሰው ሕመም ምን ዐይነት እንደ ሆነ በትክክል ለይቶ ማወቅ አይቻልም። የዳዊት ሥቃይ የተባባሰው ወዳጆቹ ሁሉ ጥለውት ስለሸሹና (ቍ11)፣ ይህንንም አጋጣሚ በመጠቀም ጠላቶቹ ሊጥሉት በማሤራቸው ነው (ቍ 12፡16፡19-20)፤ የመዝ 39-41 መግቢያ ይመ። በጥንቲቱ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት ውስጥ ይህ መዝሙር ከሰባቱ የጭንቅ ጊዜ ወይም የችግር ጊዜ መዝሙሮች ውስጥ የሚመደብ ነው (የመዝ6ን መግቢያ ይመ)። እንደ መዝ33 ሁሉ (የመዝ33 አወቃቀር ለመመልከት የመዝሙሩን የመግቢያ ማብ ይመ) የዚህም መዝሙር ርዝመት (22 ቍጥሮች አሉት) የዕብራይስጡን የፊደል ገበታ ቍጥር የተከተለ ነው። መዝሙሩ እያንዳንዳቸው አራት ስንኞች ባሏቸው አምስት አንጓዎች የተዋቀረ ሲሆን፣ እያንዳንዱም አንጓ በሁለት በሁለት ስንኞች የተቋጠረ ነው።

38ርእስ *ልመና፤* ይህ ሐረግ በሌላ ቦታ የሚገኘው በመዝ 70 ርእስ ላይ ብቻ ነው።

*38፥1-4፤* ጌታ ተግሣጹን ያቀልለትና ያነሳለት ዘንድ ያቀረበው ልመና ነው።

38፥1 *አትገሥጸኝ ...አትቅጣኝ፤* (39፥11፤ እንዲሁም የ3፥7 ማብ ይመ)። *በቍጣህ ... በመዓትህም፤* የ2፥5 ማብ ይመ።

38፥2 *ፍላጻዎችህ፤* የእግዚአብሔርን በትር በግልጽ የሚያሳይ ተለዋጭ ዘይቤ ነው (ኢዮ6፥4፤ 34፥6፤ ሰቆ3፥12፤ ሕዝ5፥16 ይመ)። *እጅህም ተጭናኛለች፤* 32፥4 እና የ32፥3-5 ማብ ይመ።

38፥3 *ዐጥንቶቼ፤* የ6፥2 ማብ ይመ።

38፥4 *ሸክምም፤* በደሉ ያደረሰበትን የሥነ ልቡና ውድቀት ብቻ ሳይሆን በቍ5-8 ላይ እንደ ተገለጸው ከባድ ሥቃይ እንደ ተጫነውም ያሳያል።

*38፥5-8፤* ሕመሙ ያስከተለበትን አካላዊና ሥነ ልቡናዊ ቀውስ ያመለክታል።

38፥8 *ከልቤም፤* የ4፥7 ማብ ይመ።

*38፥9-12፤* የሕመሙ ሥቃይ (ቍ10)፣ የወዳጆቹ ከእርሱ መራቅና (ቍ11) የጠላቶቹም ክፋት (ቍ12)፣ ክፉኛ የጐዳው መሆኑን በድጋሚ በማስታወቅ አቤቱታውን የሚያቀርብበት ክፍል ነው።

38፥10 *የዐይኔም ብርሃን ጠፍቶአል፤* የ13፥3 ማብ ይመ።

38፥11 *ከቍስሌ፤* ይህ ቃል ለምጽ ያለበትን ሰው ለማመልከት ይውላል፤ ይህ የሚያሳየው የዳዊት ወዳጆች ዳዊትን ለምጽ እንዳለበት ሰው ያገለሉት መሆኑን ነው።

*38፥12፤* የ5፥9 ማብ ይመ።

*38፥13-16፤* ጌታ ለጠላቶቹ መልስ ይስጥ ማለቱ ነው (ቍ15)፤ መስማትና መናገር እንደማይችል ሰው፣ ዳዊት ለጠላቶቹ መልስ መስጠት አቃተው (ቍ13-14)፤ ስለዚህም በእርሱ ስም እግዚአብሔር እንዲናገርለት መጠባበቅ ጀመረ (ቍ15-16)፤ 1ሳሙ 25፥32-39፤ 2ሳሙ16፥10፡12 ይመ።

38፥16 *እግሬም ሲንሸራተት ጊዜ፤* በዚህ ቦታ ይህ አባባል የሚያሳየው መዝሙረኛው የደረሰበትን ሕመም ነው (66፥9፤

[17]ልወድቅ ተቃርቤአለሁ፤
ከሥቃዬም ከቶ አልተላቀቅሁም።
[18]በደሌን እናዘዛለሁ፤
ኀጢአቴም አውካኛለች።
[19]ብርቱዎች ጠላቶቼ ብዙ ናቸው፤
ያለ ምክንያት የሚጠሉኝም ስፍር
ቍጥር የላቸውም።
[20]መልካሙን ስለ ተከተልሁ፣
በበጎ ፈንታ ክፉ የሚመልሱልኝ ጠሉኝ።
[21]እግዚአብሔር ሆይ፤ አትተወኝ፤
አምላኬ ሆይ፤ ከእኔ አትራቅ።
[22]ጌታዬ መድኀኔ ሆይ፤
እኔን ለመርዳት ፍጠን።

## መዝሙር 39

### ታላቅ እግዚአብሔር - ታናሽ ሰው

*ለመዘምራን አለቃ፣ ለኤዶታም፤ የዳዊት መዝሙር*

[1]እኔ፣ "በአንደበቴ እንዳልበድል፣
መንገዴን እጠብቃለሁ፤
ክፉዎችም በእኔ ዘንድ እስካሉ ድረስ፣
ልጓም በአፌ አስገባለሁ" አልሁ።
[2]እንደ ዲዳ ዝም አልሁ፤
ለበጎ ነገር እንኳ አፌን ዘጋሁ፤
ሆኖም ጭንቀቴ ባሰ።
[3]ልቤ በውስጤ ጋለ፤
በማሰላስልበትም ጊዜ እሳቱ ነደደ፤
ከዚያም በአንደበቴ እንዲህ ተናገርሁ፤
[4]"እግዚአብሔር ሆይ፤ የሕይወቴን ፍጻሜ፣
የዘመኔንም ቍጥር አስታውቀኝ፤
አላፊ ጠፊ መሆኑንም ልረዳ።
[5]እነሆ፤ ዘመኔን በስንዝር ለክተህ
አስቀመጥህ፤
ዕድሜዬም በፊትህ እንደ ኢምንት ነው፤
በእርግጥ የሰው ሁሉ ሕይወት ተን ነው።
ሴላ
[6]ሰው የጥላ ውልብታ ነው፤
በከንቱም ይታወካል፤
ለማን እንደሚሆን ሳያውቅ ሀብት
ንብረት ያከማቻል።
[7]"ጌታ ሆይ፤ አሁንስ ወደ ማን ልመልከት?
ተስፋዬ በአንተ ላይ ነው።
[8]ከኀጢአቴ ሁሉ አድነኝ፤
የሰነፎች መሳለቂያ አታድርገኝ።
[9]ይህን ያደረግህ አንተ ነህና፣
ዝም እላለሁ፤ አፌንም አልከፍትም።
[10]ክንድህን አንሣልኝ፤
ከእጅህ ምት የተነሣ ደክሜአለሁና።
[11]ሰዎችን ስለ ኀጢአታቸው ለመቅጣት
ትገሥጻቸዋለህ፤
ሀብታቸውንም ብል እንደ በላው
ታደርጋለህ፤
በእርግጥ ሰው ሁሉ ተን ብቻ ነው።
ሴላ

38፥17 ቍ7፤ኢዮ 6፥10፤መዝ37፥24
38፥18 ዘሌ26፥40
38፥19 መዝ18፥17፤25፥19፤35፥19
38፥20 ዘፍ44፥4፤ መዝ54፥5፤59፥10፤119፥23፤1ዮሐ3፥12
38፥21 መዝ10፥1፤22፥11፤27፥9፤35፥22፤71፥12:18፤119፥8
38፥22 1ዜና16፥35፤መዝ22፥19፤40፥13
39፥1 1ነገ2፥4፤ኢዮ 1፥22፤6፥24፤መዝ34፥13፤119፥9:59፤ምሳ20፥11፤ያዕ1፥26፤3፥2
39፥2 ቍ9፤ኢዮ 31፥34፤መዝ6፥3፤25፥17፤31፥10፤77፥4
39፥3 መዝ1፥2፤48፥9፤77፥12፤119፥15፤ኤር5፥14፤20፥9፤23፥29፤ሉቃ24፥32
39፥4 ዘፍ47፥9፤ ኢዮ7፥7፤14፥2:5
39፥5 ኢዮ7፥7፤10፥20፤መዝ62፥9፤89፥45፤102፥23
39፥6 ኢዮ8፥9፤27፥17፤መዝ102፥11፤127፥2፤መክ6፥12፤ሉቃ12፥20፤ያዕ1፥11፤4፥14
39፥7 መዝ9፥18፤25፥5
39፥8 ዘዳ28፥37፤ መዝ6፥4፤32፥1፤51፥1:14፤69፥7፤79፥4፤ኢሳ 43፥28፤53፥5:8:10፤ዳን 9፥16 39፥9 ቍ2፤መዝ 38፥13፤ኢሳ38፥15 39፥10 ዘፀ9፥3፤2ዜና 21፥14፤ሕዝ 7፥9፤24፥16 39፥11 ዘዳ28፥20፤ኢዮ7፥7፤13፥28፤መዝ 90፥7፤94፥10፤ኢሳ26፥16፤51፥8፤66፥15፤ሕዝ5፥15፤ሉቃ12፥33፤ያዕ5፥2፤ 2ጴጥ2፥16

94፥18፤ 121፥13 ይመ)፤ ይህንንም የተናገረው የግል ሕይወቱ በተናጋበት ወይም አስቸጋሪ ሁኔታ በደረሰበት ጊዜ ነው።

*38፥17-20፤* ጤናውን እያጣ በሄደ ቍጥር፣ የጠላቶቹ ጕልበት እያየለ መጣ።

38፥17 *ልወድቅ፤* ሞት የከበበው መሰለው (የ13፥4 ማብ ይመ)።

*38፥18፤* ቍ3-4፤ መዝ32 ይመ።

*38፥19-20፤* ኀጢአት በመሥራቱ ጌታን በድሎአል፤ ነገር ግን አሁን በሚያጠቁት ጠላቶቹ ላይ አንዳች በደል አላደረሰም (የ35፥19 ማብ ይመ)።

38፥20 *መልካሙን፤* በሥነ-ምግባር ረገድ ነቀፋ የሌለበት ማለት ነው (34፥14 ይመ)።

*38፥21-22፤* በመደምደሚያ ላይ በድጋሚ የቀረበ አቤቱታ ነው።

38፥21 *ከእኔ አትራቅ፤* ሆን ተብሎ የሚሠራ ኀጢአት ከሚያስከትለው አስከፊ ነገር ውስጥ አንዱ ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረትን ማጣት ነው (ከ22፥19፤ 35፥22፤ 71፥12 ጋር ያነጻጽሩ)፤ የእግዚአብሔርን ምሕረት ከተረዱና የመንፈስ ቅዱስም ማደሪያ ከሆኑ በኋላ ሆን ብሎ ኀጢአት መሥራት እጅግ አሳዛኝና መራራም ተሞክሮ ነው።

*መዝሙር 39፤* መዝሙረኛው የሰው ሕይወት እጅግ ከንቱና ምናምንቴ በመሆኑ የተሰማውን ጥልቅ ሐዘን የሚገልጥበት ጸሎት ነው። ይህንንም የተረዳው በፈጸመው ኀጢአት ምክንያት (ቍ8) እግዚአብሔር በሕመም ስለገሠጸው ነው (ቍ10-11)። መዝሙር 38 የሚናገረው መዝሙረኛው በጠላቶቹ ፊት ዝም ስለማለቱ ሲሆን መዝሙር 39 ደግሞ በእግዚአብሔር ፊት ዝም ስለ ማለቱ ነው። ሁለቱም መዝሙሮች በሕመም ጊዜ (እግዚአብሔር "በገሠጸው" ጊዜ ቍ11፤ 38፥1) የቀረቡ ጸሎቶች ናቸው፤ ሁለቱም መዝሙሮች በደለኛነትን ይቀበላሉ፤ በእግዚአብሔር መታመን ተገቢ መሆኑንም ያስገነዝባሉ። የመዝ40 መግቢያን ይመ። ከዚህም በተጨማሪ ይህ መዝሙር ከመዝ90 ጋር በብዙ ረገድ ተወራራሽነት አለው፤ እንዲሁም መዝሙር 49 ይመ።

39ርእስ *ለመዘምራን አለቃ፤* የመዝ4 የርእስ ማብ ይመ። *ኤዶታም፤* ዳዊት ከነበሩት ሦስት የመዘምራን አለቃ ውስጥ አንዱ ነው (1ዜና16፥41-42፤ 25፥1:6፤ 2ዜና5፥12፤ በ2ዜና35፥15 ላይ "ባለ ራእዩ" ተብሎአል)። ኤዶታም ምናልባት በ1ዜና6፥44 እና በ15፥19 ላይ "ኤታን" የተባለው ሊሆን ይችላል፤ ይህ ከሆነ ደግሞ አሳፍ የጌድሶን ቤተ ሰብ ተጠሪ ኤማን ደግሞ የቀዓት ቤተ ሰብ ተጠሪ እንደ ሆን ሁሉ፣ ኤዶታምም የሜራሪ ቤተ ሰብ ተጠሪ ሊሆን ይችላል፤ እነዚህ ሁሉ የሌዊ ወንዶች ልጆች ናቸው (1ዜና 6፥16:33:39:43-44 ይመ)። የመዝ62፤ 77፤ 89 ርእስን ይመ።

*39፥1-3፤* የመዝሙሩ መግቢያ ነው፤ ምንም ነገር ላለመናገር ቢወስንም፣ ሥቃዩን እስከ መጨረሻው አፍኖ መቀመጥ አልቻለም።

*39፥1፤* የክፉዎች ንግግር አስቈጥቶት መጥፎ ነገር እንዳይናገር ለአንደበቱ ልጓም አደረገለት (መዝ 73 ይመ)።

*39፥2-3፤* ታምቆ የተቀመጠ ሥቃይ ሕመምን ያባብሳል እንጂ ምንም መፍትሔ አያመጣም (ኤር20፥9)።

*39፥4-6፤* የሰው የሕይወት ዘመን አጭር መሆኑን እንዲያስተውልና ይህንንም በጸጋ እንዲቀበል የቀረበ ጸሎት ነው።

39፥4 *የዘመኔንም ቍጥር፤* 78፥39 እና የ37፥20 ማብ ይመ።

39፥5 *በፊትህ እንደ ኢምንት፤* 90፥4 ይመ። *ተን፤* ቍ11፤ 144፥4፤ ኢዮ14፥2፤ መክ6፥12 ይመ።

*39፥6፤* የመጽሐፈ መክብብ ማጠቃለያ በመሆን ሊያገለግል ይችላል።

*39፥7-11፤* በተሰበረ ልብ የቀረበ ጸሎት ነው፤ መዝሙረኛው የሚለምነው እግዚአብሔር አለንጋውን እንዲያነሳለት ብቻ ነው።

39፥8 *አድነኝ፤* ከጠላቶቼ ታደገኝ ማለቱ ነው። *የሰነፎች መሣለቂያ፤* እግዚአብሔር ካልታደገው በቀር በዐመፀኞችና በሰነፎች እጅ (14፥1 ይመ) መሣለቂያ መሆኑ አይቀርም (22፥7-8፤ 69፥6-12 ይመ)።

39፥10 *ከእጅህ ምት፤* 32፥4፤ 38፥2 ይመ።

39፥11 *ለመቅጣት ትገሥጻቸዋለህ፤* 6፥1፤ 38፥1 ይመ። *በእርግጥ ተን፤* ኢሳ2፥22 እና ማብ ይመ፤ ቍ1፤ 144፥4፤ ኢዮ14፥2፤ መክ6፥12 ይመ።

*39፥12-13፤* በተሰበረ ልብ የቀረበው ጸሎት ከቀድሞው

[12]"እግዚአብሔር ሆይ፤ ጸሎቴን ስማ፤
ጩኸቴን አድምጥ፤
ልቅሶዬንም ቸል አትበል፤
በአንተ ፊት እኔ መጻተኛ ነኝና፤
እንደ አባቶቼም እንግዳ ነኝ።
[13]ላለመመለስ ከመሰናበቴ በፊት፣
ዳግመኛ ደስ ይለኝ ዘንድ ዐይንህን
ከላዬ አንሣ።

## መዝሙር 40
### የምስጋናና የርዳታ ልመና ጸሎት

40፥13-17 ተጓ ምብ-መዝ70፥1-5

ለመዘምራን አለቃ፤ የዳዊት መዝሙር

[1]እግዚአብሔርን ደጅ ጠናሁት፤
እርሱም ዘንበል አለልኝ፤ ጩኸቴንም
ሰማ።
[2]ከሚውጥ ጕድጓድ፣
ከሚያዘቅጥ ማጥ አወጣኝ፤
እግሮቼን በዐለት ላይ አቆመ፤
አካሄዴንም አጸና።
[3]ለአምላካችን የሚሆን ውዳሴ፣
አዲስ ዝማሬን በአፌ ላይ አኖረ፤
ብዙዎች ያያሉ፤ ይፈራሉም፤
በእግዚአብሔር ይታመናሉ።
[4]እግዚአብሔርን መታመኛው ያደረገ፣

39፥12 ዘኍ23፥41 47፥9፤ዘሌ25፥23፤ዘዳ 1፥45፤2ነገ20፥5፤1ዜና 29፥15፤መዝ17፥1፤ ዕብ 11፥13
39፥13 ኢዮ10፥21
40፥1 መዝ6፥9፤ 31፥22፤34፥15፤37፥7 ፤116፥1፤145፥19
40፥2 ኢዮ9፥31፤ 30፥19፤መዝ7፥15፤27 ፥5፤31፥8፤69፥14
40፥3 ዘፀ14፥31፤መዝ 28፥7፤52፥6፤64፥9፤9 6፥1፤ራእ5፥9
40፥4 ዘዳ31፥20፤ መዝ4፥2፤26፥1፤34፥8 ፤84፥12፤101፥5፤138 ፥6፤ምሳ3፥34፤16፥5፤ ኢሳ65፥5፤1ጴጥ5፥5
40፥5 ዘዳ4፥34፤ መዝ 71፥15፤75፥1፤ 105፥5፤136፥4፤ 139፥17፡18
40፥6 ዘፀ21፥6፤1ሳሙ 15፥22፤መዝ50፥8፤ 51፥16፤ኢሳ1፥11፤ ኤር 6፥20፤ሆሴ6፥6፤ አሞ5፥22
40፥7 ኢዮ19፥23፤ ኤር36፥2፤45፥1፤ሕዝ 2፥9፤ዘካ5፥1
40፥8 ዘዳ6፥6፤

ወደ ትዕቢተኞች የማይመለከት፣
የሐሰት አማልክትን[ሠ] ወደሚከተሉት
የማያይ፣
ሰው ብፁዕ ነው።
[5]እግዚአብሔር አምላኬ ሆይ፤
አንተ ያደረግኸው ድንቅ ነገር ብዙ
ነው፤
ለእኛ ያቀድኸውን፣
ሊዘረዝርልህ የሚችል ማንም የለም፤
ላውራው ልናገረው ብል፣
ስፍር ቍጥር አይኖረውም።
[6]መሥዋዕትንና ቍርባንን አልፈለግህም፤
ጆሮቼን ግን ከፈትህ፤[ጨ]
የሚቃጠል መሥዋዕትን፣
የኀጢአትንም መሥዋዕት አልሻህም።
[7]እኔም እንዲህ አልሁ፤ "እነሆ፤ መጥቻለሁ፤
ስለ እኔ በመጽሐፍ ተጽፎአል፤
[8]አምላኬ ሆይ፤ ፈቃድህን ላደርግ እሻለሁ፤
ሕግህም በልቤ ውስጥ አለ።"
[9]በታላቅ ጉባኤ ውስጥ ጽድቅን አበሠርሁ፤

ኢዮ 22፥22፤ማቴ26፥39፤ ሮሜ7፥22፤ዕብ10፥5-7
40፥9 ኢሱ22፥22፤ መዝ22፥25፡31

[ሠ]4 ወይም *ሐሰትን ወደሚከተሉት* ተብሎ መተርጐም ይችላል።
[ጨ]6 ዕብራይስጡ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ግን፣ *አካልን ግን አዘጋጀህልኝ* ይላል።

ይልቅ አጅግ በተሰበረ ልብ በድጋሜ ቀርቦአል።

39፥12 *መጻተኛ እንግዳ፤* በዚህ ዓለም በእግዚአብሔር ፊት ሲመላለስ ኑሮውን ሁሉ የሚያየው እንደ ስደተኛ ወይም እንደ መጻተኛ ነው።

39፥13 *ዐይንህን ከላዬ አንሣ፤* ኢዮ7፥17-19፤ 10፤20-21፤ 14፥6 ይመ። *ዳግመኛ ደስ ይለኝ ዘንድ፤* ኢዮ9፥27፤ 10፥20 ይመ። *ከመረሳቴ በፊት፤* ከሞት ባሻገር ስላለው ዓለም።

*መዝሙር 40፤* አስጨናቂ መከራ በከበበው ጊዜ ያቀረበው ጸሎት ነው። የሐዘኑ መንሥኤ ምን እንደ ሆነ በውል አልተጠቀሰም፤ ዳዊት ግን በመዝ38-39 እና 41 ላይ እንዳስታወቀው፣ ይህ ሁሉ መከራ የደረሰበት በፈጸመው ኀጢአት ምክንያት መሆኑን (ቍ12 ይመ) ተገንዝቦአል፤ (የመዝ39 እና 41 መግቢያን ይመ)። ሥቃዩ የተባባሰበት ጠላቶቹ በእርሱ ሥቃይ በመደሰታቸውና በመጓደዳቸው ምክንያት ነው፤ ይህ ርእስ ጕዳይ በዚህ መዝሙርና በመዝሙር 38-39 ላይ በዐቢይ ርእስ ጕዳይነት ተንጸባርቆአል (የመዝ6ን መግቢያ ይመ)። ጸሎቱ የሚጀምረው እግዚአብሔር ከዚህ ቀደም ስላደረገለት ምሕረት ምስጋና በማቅረብና (ቍ1-5) ለእግዚአብሔርም ያሳየውን ታማኝነት በመግለጽ ነው (ቍ6-10)። መዝሙረኛው እግዚአብሔር ረዳቱ እንዲሆን ልመናውን የሚያቀርበው እነዚህን ሁለት ጕዳዮች መሠረት በማድረግ ነው (ቍ11-17)። በመዝ44 እና 89 ላይ የተመለከተውን ረዘም ያለ የጸሎት መግቢያ ይመ። መዝ70 በዚህ ምዕራፍ በቍ13-17 ላይ ከሚገኘው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይነት አለው።

40ርእስ፤ *ለመዘምራን አለቃ፤* የመዝ 4 የርእስ ማብ ይመ።

*40፥1-5፤* እግዚአብሔር ከዚህ ቀደም ስላደረገው ምሕረት የቀረበ ምስጋና ነው (የመዝ9ን መግቢያ ይመ)።

*40፥1-3፤* ዳዊት በገጠመው ታላቅ መከራ ጊዜ እግዚአብሔር ያሳየው ቸርነት ለእግዚአብሔር ምስጋና እንዲያቀርብና ሌሎችንም ወደ እምነት እንዲመራ አነቃቅቶታል (የ7፥17 እና 9፥1 ማብ ይመ)።

*40፥2፤* መዝ 30፥1 እና ማብ ይመ።

40፥3 *አዲስ ዝማሬን፤* የ33፥3 ማብ ይመ። *ብዙዎች ያያሉ፤* ዳዊት ካቀረበው ምስጋና የተነሣ ነው (18፥49፤ 22፥22-31 ይመ፤ እንዲሁም የ9፥1 ማብ ይመ)። *ይፈራሉም፤* የ34፥8-14 ማብ ይመ።

*40፥4-5፤* እግዚአብሔርን በእርሱ ለሚታመኑ ሁሉና (ቍ4) ለሕዝቡም ለእስራኤል (ቍ5) ያለውን ቸርነት ያሳያል።

*40፥4፤* ኤር17፥7 ይመ። በእርሱ የሚታመኑ ሁሉ የተባረኩ በመሆናቸው፣ ለጌታ የቀረበ ምስጋና ነው (32፥1-2፤ 146፥5 ይመ)። *ትዕቢተኞች፤* የ31፥23 ማብ ይመ። *ብፁዕ፤* የ1፥1 ማብ ይመ።

40፥5 *ድንቅ ነገር፤* የ9፥1 ማብ ይመ። *ያቀድኸውን፤* እግዚአብሔር ለእስራኤል ያሰበውንና ያቀደውን ነገር ሁሉ የሚያደርገው አስቀድሞ በወሰነው መሠረት ነው (ኢሳ 25፥1፤ 46፥10-11 ይመ)።

*40፥6-8፤* ዳዊት ለእግዚአብሔር ፈቃድ ምን ያህል ተገዥ እንደ ሆነ ያሳያል፤ የዕብ10፥5-10 ጸሓፊ በዚህ ቦታ የተጠቀሱትን ነገሮች ለክርስቶስ ተጠቅሞባቸዋል (ማብ በዚያው ቦታ ይመ)።

40፥6 *መሥዋዕትንና ቍርባንን ... አልሻህም፤* መዝሙረኛው እግዚአብሔር በሕጉ ላይ ያስታወቃቸው የመሥዋዕትና የመንጻት ሥርዐቶች በራሳቸው ብቁ እንዳልሆኑና ራስን ከልብ ለእግዚአብሔር መስጠትንና ለእርሱም ብቻ ታማኝ መሆንን ሊተኩ እንደማይችሉ ተረድቶአል (1ሳሙ15፥22፤ ኢሳ1፥11-17፤ ኤር7፥22-23፤ ሚክ6፥6-8)። ልክ እንዲሁ የአዲስ ኪዳን አማኝ ራሱን ከልብ ለእግዚአብሔር ሳይሰጥ የውሃ ጥምቀትን ሊወስድ፣ የጌታ እራትን ሊካፈልና በመዝሙርና በአምልኮም ሥርዐቶች ላይ ንቁ ተሳታፊ ሊሆን ይችላል። ነገር ግን የትኛውም ሃይማኖታዊ ሥርዐት ለእግዚአብሔር ያለንን ታማኝነትና ታዛዥነት ሊተካ አይችልም፤ ከእምነት የሆነ መታዘዝ ከሌለ ሁሉም ሥርዐት ብቻ ሆኖ ይቀራል (ከሮሜ1፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

40፥7 *እነሆ መጥቻለሁ፤* ምናልባት ዳዊት በንግሥናው ወቅት ራሱን ለጌታ አሳልፎ የሰጠበትን ሁኔታ ሊያመለክት ይችላል። *ስለ እኔ በመጽሐፍ ተጽፎአል፤* አንዳንዶች በዘዳ 17፥14-15 ላይ ያለውን ትንቢት ሳያመለክት አይቀርም ይላሉ፤ ይሁን እንጂ የዚህ መዝሙር ዐውደ ንባብ በእጅጉ የሚያመለክተው "መጽሐፍ" የሚለው ቃል አንድ ንጉሥ በሚነግሥበት ወቅት የግዛቱ መተዳደሪያና ቃል ኪዳንም አድርጎ የሚይዘውን የሕጉን ቅጅ ነው (ዘዳ17፥18-20፤ 2ነገ11፥12 ይመ፤ ከ1ነገ2፥3 ጋር ያነጻጽሩ)።

40፥8 *ሕግህም በልቤ ውስጥ አለ፤* እግዚአብሔር ሊያየው የሚመኘው "ከእምነት የሆነ መታዘዝ" ፈቃዱን ለማድረግ ደስ የሚለውን እምነትና ሕጉንም በልቡ ውስጥ ለመሰወር ደስ የሚለውን እምነት ነው (ከ119፥11፤ ከዮሐ15፥17 ጋር ያነጻጽሩ)።

*40፥9-10፤* የዳዊት ሕይወት በምስጋና መሞላቱንና የእግዚአብሔርንም ታማኝነትና ምሕረት ዘወትር ለማወጅ መነሣቱን ያሳያል። እግዚአብሔር ከእንስሳት መስዋዕት አብልጦ የሚወደው እንዲህ ያለውን መሥዋዕት ነው (50፥7-15፡23 ይመ)።

40፥9 *በታላቅ ጉባኤ፤* የ1፥5 እና የ9፥1 ማብ ይመ። *ጽድቅን፤* የ4፥1 ማብ ይመ። *አበሠርሁ፤* 68፥11፤ 96፥2 ይመ፤ የምሥራች ቃል አድርጌ እናገረዋለሁ ማለቱ ነው (1ነገ1፥42፤ ኢሳ40፥9፤

እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ
እንደምታውቀው፣
ከንፈሮቼን አልገጠምሁም::
[10]ጽድቅህን በልቤ አልሸሸግሁም፤
ታማኝነትህንና ማዳንህን እናገራለሁ፤
ምሕረትህንና እውነትህን፣
ከታላቅ ጉባኤ አልደበቅሁም::

[11]እግዚአብሔር ሆይ፤ ምሕረትህን
አትንፈገኝ፤
ቸርነትህና እውነትህ ዘወትር ይጠብቁኝ፤
[12]ስፍር ቍጥር የሌለው ክፋት ከቦኛልና፤
የኀጢአቴ ብዛት ስለ ያዘኝ ማየት
ተስኖኛል፤
ከራሴ ጠጕር ይልቅ በዝቶአል፤
ልቤም ከድቶኛል::

[13]እግዚአብሔር ሆይ፤ ታድነኝ ዘንድ
ፈቃድህ ይሁን፤
እግዚአብሔር ሆይ፤ እኔን ለመርዳት
ፍጠን::
[14]ነፍሴን ለመንጠቅ የሚፈልጉ፣
ይፈሩ፤ ይዋረዱም፤
ጕዳቴንም የሚሹ፣
ተዋርደው በመጡበት ይመለሱ::
[15]በእኔ ላይ፣ "እሰይ! እሰይ!" የሚሉ፣
በራሳቸው እፍረት ይደንግጡ::
[16]አንተን የሚፈልጉ ሁሉ ግን፣
ሐሤት ያድርጉ፤ በአንተም ደስ
ይበላቸው፤
ዘወትር የአንተን ማዳን የሚወዱ፣
"እግዚአብሔር ከፍ ከፍ ይበል" ይበሉ::

40፥10 መዝ22፥22 ፤89፥1
40፥11 መዝ26፥3፤ 61፥7፤ምሳ20፥28፤ዘካ 1፥12
40፥12 መዝ25፥17 ፤38፥4፤65፥3፤69፥4፤7 3፥26
40፥13 መዝ22፥19 ፤38፥22
40፥14 1ሳሙ20፥1 ፤አስ9፥2፤መዝ35፥4፡ 26
40፥15 መዝ35፥21
40፥16 ዘጸ4፥29፤ 1ዜና28፥9፤መዝ9፥2፡ 10፤35፥27፤119፥2
40፥17 መዝ18፥2፤ 20፥2፤86፥1፤109፥22 ፤119፥60፤144፥3
41፥1 ዘጸ14፥29፤ ኢዮ24፥4፤25፥17
41፥2 ዘጸ6፥24፤ዕዝ 9፥9፤መዝ12፥5፤32፥7 ፤37፥22፤71፥20፤119 ፥88፡159፤138፥7፤14 3፥11
41፥3 2ሳሙ13፥5 ፤2ነገ1፥4፤መዝ6፥6
41፥4 ዘጸ32፥39 ፤6፥2፤9፥13፤51፥4
41፥5 መዝ38፥12
41፥6 ዘሌ19፥16፤ መዝ12፥2፤101፥7፤ ምሳ26፥24፤ማቴ5፥11

[17]እኔ ድኻና ችግረኛ ነኝ፤
ጌታ ግን ያስብልኛል::
አንተ ረዳቴና አዳኜ ነህ፤
አምላኬ ሆይ፤ አትዘግይ::

## መዝሙር 41

### የሕመምተኛና የብቸኛ ሰው ጸሎት

ለመዘምራን አለቃ፤ የዳዊት መዝሙር

[1]ለድኾች የሚያስብ ሰው ምስጉን ነው፤
እርሱንም እግዚአብሔር በክፉ ቀን
ይታደገዋል::
[2]እግዚአብሔር ይጠብቀዋል፤ በሕይወትም
ያኖረዋል፤
በምድርም ላይ ይባርከዋል፤
ለጠላቶቹም ምኞትም አሳልፎ
አይሰጠውም::
[3]ታሞ ባለበት ዐልጋ ላይ እግዚአብሔር
ይንከባከበዋል፤
በበሽታውም ጊዜ መኝታውን
ያነጥፍለታል::
[4]እኔም፣ "እግዚአብሔር ሆይ፤ ምሕረት
አድርግልኝ፤
አንተን በድያለሁና ነፍሴን ፈውሳት"
አልሁ::
[5]ጠላቶቼ በክፋት በመናገር፣
"የሚሞተው መቼ ነው? ስሙስ
የሚደመሰሰው ምን ቀን ነው?"
ይላሉ::
[6]ሊጠይቀኝ የሚመጣ ቢኖር፣
በልቡ ስድብ እያጠራቀመ፣ ከዐንገት
በላይ ይናገራል፤

---

41፥27፤ 52፥7፤ 61፥1 ይመ):: *ከንፈሮቼንም አልገጠምሁም፤* እግዚአብሔርን ከማመስገን አይቈጠብም (38፥13-16፤ 39፥1 እና ማብ ይመ)::

40፥10 *በልቤ፤* የ4፥7 ማብ ይመ:: *ምሕረትህንና እውነትህን፤* የ26፥3 ማብ ይመ::

*40፥11-17፤* ርዳታን ለማግኘት የቀረበ ጸሎት ነው::

40፥11 *ቸርነትህና እውነትህ፤* በቤተ መቅደስ ውስጥ ለሁሉም ያውጅ የነበረውን ማለት ነው (ቍ10እና ማብ ይመ)::

40፥12 *የኀጢአቴ ብዛት ስለያዘኝ፤* "ስፍር ቍጥር የሌለው ችግር እንደ ከበበው" ሁሉ የኀጢአትም ብዛት አስጨንቆታል (መዝ38-39 እና መግቢያቸውን ይመ):: *ማየት ተስኖኛል፤* የ13፥3 ማብ ይመ:: *ከራሴ ጠጕር ይልቅ፤* ማቴ10፥30፤ ሉቃ 12፥7 ይመ:: *ልቤም፤* የ4፥7 ማብ ይመ::

*40፥14-15፤* በመዝ38፥12፤ 39፥8፤ 41፥5፡7 ላይ እንደ ተገለጸው በሚያስጨንቅ ችግር ውስጥ እያለ እንኳን ጠላቶቹ አያርፉለትም (የ5፥9 ማብ ይመ):: በዳዊት መዝሙር ውስጥ ይህ ሁኔታ በተደጋጋሚ ተወስቶአል:: እርሱን ለማዋረድ ደፋ ቀና የሚሉ ሁሉ እነርሱም ይዋረዱ (የ5፥10 ማብ ይመ)::

40፥15 *እሰይ! እሰይ!* የ3፥2 ማብ ይመ::

40፥17 *ድኻና ችግረኛ፤* የእግዚአብሔርን ርዳታ በብርቱ ይሻል (የ34፥6 ማብ ይመ)::

*መዝሙር 41፤* ዳዊት በጠና በታመመ ጊዜ ምሕረትን ያገኝ ዘንድ ያቀረበው ጸሎት ነው፤ ሕመሙ ከፈጸመው ኀጢአት ጋር ዝምድና እንዳለው ተገንዝቦአል (ቍ4)፤ የመዝሙር 38-40 መግቢያን ይመ:: ጠላቶቹ ብቻ ሳይሆኑ "ወዳጆቹ" (ቍ9) የሚላቸውም እንኳ ሞቱን ይመኙለት ነበር (የ5፥9 ማብ ይመ)፤ ከሁሉ ግን የልብ ወዳጁ ያላቸው ሳይቀሩ በእርሱ ላይ በባላጋራነት መነሣታቸው እጅጉን አሳዝኖታል (የ31፥11-12 ማብ ይመ):: ይህ መዝሙር ተመሳሳይ ፍሬ ሐሳብ ላላቸው አራት መዝሙሮች መደምደሚያ ከመሆኑም በላይ "የአንደኛ መጽሐፍ" መዝጊያ በመሆንም ያገለግላል (ይህ አንደኛ መጽሐፍ "ምስጉን ነው" በሚለው ሐረግ ጀምሮ በዚሁ ይደመድማል):: ባወቃቀር ረገድ ሲታይ ይህ መዝሙር እኩኩል ሲሆን፣ እያንዳንዳቸው ሦስት ሦስት ስንኞች ባሏቸው በአራት አንጓዎች የተከፈለ ነው:: አንደኛውና አራተኛው አንጓ የመዝሙረኛው ጸሎት ከልብ የቀረበ መሆኑን ያሳያሉ፤ ሁለተኛውና ሦስተኛው አንጓ የጸሎቱን ፍሬ ሐሳብ የበለጠ ያብራራሉ:: ቍ13 የዚህ መዝሙር አካል ባይሆንም "አንደኛ መጽሐፍን" በምስጋና ይደመድማል (የቍ13 ማብ ይመ)::

41ርእስ *ለመዘምራን አለቃ፤* በመዝሙር 4 ርእስ ላይ የተሰጠውን ማብ ይመ::

*41፥1-3፤* እግዚአብሔር ጤናውን እንደሚመልስለት በእርግጠኛነት የተናገረበት ቦታ ነው::

41፥1 *ለድኾች የሚያስብ ምስጉን ነው፤* በተለይ ንጉሥ ከሆነ ለደካሞች ቋሚ ጠበቃ መሆን አለበት (72፥2፡4፡12-14፤ 82፥3-4፤ ምሳ29፥14፤ 31፥8-9፤ ኢሳ11፥4፤ ኤር22፥16 ይመ):: *ምስጉን፤* የ1፥1 ማብ ይመ:: እግዚአብሔር "ለደካሞችና ለረዳት የለሾች ልዩ ጥንቃቄ ያደርግላቸዋል፤ ለእንዲህ ላሉ ወገኖች የሚራሩትንም ይባርካቸዋል፤ የቍ1-3 ሐሳብን ስናብራራው እንዲህ ማለት ይሆናል "ምሕረት የሚያደርጉ ምስጉኖች ናቸው ይማራሉና" (ማቴ5፥7)፤ ከእግዚአብሔር ርኅራኄ ጋር በመተባበር ሌሎችን በችግራቸው የምንረዳ ከሆነ እኛም መከራ በገጠመን ጊዜ እግዚአብሔር ይረዳናል (ቍ1)፣ ከጕዳት ይጠብቀናል (ቍ2)፣ ይባርከናል (ቍ2)፣ የሰይጣንን ኀይልና የጠላቶቻችንን ዛቻ ይደመስስልናል (ቍ2)፣ በታመምንም ጊዜ ከአጠገባችን ሆኖ ፈውስን ይሰጠናል (ቍ3 ይመ፤ ከ72፥2፡4፡12፤ ከዘጸ15፥7-11፤ ከምሳ 29፥14፤ ከኢሳ11፥4፤ ከኤር22፥16 ጋር ያነጻጽሩ)::

*41፥4-6፤* እግዚአብሔር ምሕረት እንዲያደርግና ፈውስም እንዲሰጥ የሚያሳስብ ጽሎት ነው::

41፥4 *በድያለሁና፤* የ32፥3-5 ማብ ይመ::

41፥5 *የሚሞተው መቼ ነው?* የ3፥2 ማብ ይመ:: *ስሙስ የሚደመሰሰው፤* የ9፥5 ማብ ይመ::

41፥6 *ሊጠይቀኝ፤* ታሞ በተኛ ጊዜ ሊጎበኘው የመጣውን ማለት ነው:: *ወሬም ይነዛል፤* የልብ ወዳጁ እንደ ሆነ ሰው ይናገ

ወጥቶም ወሬ ይነዛል።

[7]ጠላቶቼ ሁሉ ግንባር ፈጥረው
ይንሾካሾኩብኛል፤
እንዲህ እያሉም፣
የከፋ ነገር በላዬ ያውጠነጥናሉ፤
[8]"ክፉ ደዌ ይዞታል፤
ከእንግዲህም ከተኛበት አይነሣም።"
[9]እንጀራዬን ተካፍሎኝ የበላ፣
የምተማመንበትም የቅርብ ወዳጄ፣
በእኔ ላይ ተረከዙን አነሣ።

[10]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ ግን ምሕረት
አድርግልኝ፤
የእጃቸውን እንድከፍላቸው አስነሣኝ።
[11]ጠላቴ በላዬ ድል አላገኘምና፣
እንደ ወደድኸኝ በዚህ አወቅሁ።
[12]ስለ ጭንቀቴ ደግፈህ ይዘኸኛል፤
በፊትህም ለዘላለም ታኖረኛለህ።

[13]የእስራኤል አምላክ *እግዚአብሔር*፣
ከዘላለም እስከ ዘላለም የተባረከ ይሁን፤
አሜን፤ አሜን።

**ሁለተኛ መጽሐፍ**
**ከመዝሙር 42-72**

**መዝሙር 42[ሀ]**

**በስደት ላይ ያለ ሌዋዊ ልቅሶ**

*ለመዘምራን አለቃ፤ የቆሬ ልጆች ትምህርት።*

[1]ዋላ የምንጭ ውሃ እንደምትናፍቅ፣
አምላክ ሆይ፤ ነፍሴም እንዲሁ አንተን
ትናፍቃለች።
[2]ነፍሴ አምላክን፣ ሕያው አምላክን ተጠማች፤
መቼ ነው ደርሼ፣ የአምላክን ፊት
የማየው?
[3]ሰዎች ቀኑን ሙሉ፣
"አምላክህ የት አለ?" ባሉኝ ቍጥር፣
እንባዬ ቀንና ሌሊት፣
ምግብ ሆነኝ።
[4]ነፍሴ በውስጤ እየፈሰሰች፣
እነዚህን ነገሮች አስታወስሁኝ፤
ታላቅ ሕዝብ ወደ እግዚአብሔር ቤት እየመራሁ፣
በእልልታና በምስጋና መዝሙር፣
በአእላፍ ሕዝብ መካከል፣
እንዴት ከሕዝቡ ጋር እሄድ እንደ
ነበር ትዝ አለኝ።
[5]ነፍሴ ሆይ፤ ለምን ትተክዢያለሽ?
ለምንስ በውስጤ ትታወኪያለሽ?

41፥7 መዝ71፥10
41፥8 2ነገ1፥4
41፥9 ዘኍ30፥2፤ 2ሳሙ15፥12፤ኢዮ 19፥14:19፤መዝ55፥ 20፤89፥34፤ማቴ26፥ 23፤ሉቃ22፥21፤ዮሐ 13፥18
41፥10 ቍ4፤2ሳሙ 3፥39፤መዝ3፥3፤9፥13
41፥11 ዘኍ14፥8፤ መዝ25፥2
41፥12 ኢዮ4፥7፤ መዝ18፥35፤21፥6፤25 ፥21፤37፥17፤61፥7፤6 3፥8
41፥13 ዘፍ24፥27፤ መዝ72፥18:19፤89፥5 2፤106፥48
42፥1 ዘዳ10፥7ኢዮ 19፥27፤መዝ18፥33፤ 119፥131፤ኢል1፥20
42፥2 ኢሱ3፥10፤ 1ሳሙ14፥39፤መዝ43 ፥4፤63፥1፤84፥7፤143፥ 6፤ማቴ16፥16፤ሮሜ 9፥26
42፥3 ቍ10፤ኢዮ 3፥24፤መዝ79፥10፤11 5፥2፤ኢል2፥17፤ሚክ 7፥10
42፥4 ኢሱ6፥5፤ 1ሳሙ1፥15፤ዕዝ3፥13 ፤መዝ35፥18፤ 55፥14 ፤95፥2፤100፥4፤109፥30፤122፥1፤147፥7፤ኢሳ2፥2፤30፥29፤ዮና2፥9
42፥5 ኢዮ20፥2፤መዝ9፥1፤18፥46፤25፥5፤38፥6፤71፥14፤77፥3፤ ሰቆ3፥20፤ማቴ 26፥38

[ሀ]ም42 በብዙ የዕብራይስጥ ቅጆች መዝሙር42 እና 43 አንድ መዝሙር ነው።

ራል። *በልቡ፤* የ4፥7 ማብ ይመ።

*41፥7-9፤* ጠላቶቹና ወዳጁ ነን የሚሉ ሁሉ በአንድነት እንደተነሱበት የሚናገርበት ክፍል ነው።

41፥9 *እንጀራዬን ተካፍሎኝ፤ ... የምተማመንበት ወዳጄ፤* ከንጉሥ ጋር በአንድ ማዕድ የሚሳተፍ ሰው የተከበረና የታመነ ወዳጅ ነው (የ31፥11-12 ማብ ይመ)። መዝሙረኛው በዚህ ቦታ የሚናገረው ወዳጅነቱን በቃል ኪዳን ያተመውን ሰው ሳይሆን አይቀርም (የ23፥5 ማብ ይመ)። ኢየሱስ በዚህ ቍጥር ላይ የተመለከተውን ከራሱ ሕይወት ጋር እንዴት እንዳገናኘው ዮሐ13፥18 ይመ። እንደ ንጉሥ ዳዊት ሁሉ ከዳዊት ወገን የሆነው ይህ ታላቅ ልጅ ከሰዎች ጥላቻ ደርሶበታል፤ ታማኝ ወዳጆቼ የሚላቸውም ከድተውታል፤ በዚህም የአባቱን የዳዊት መከራ ተካፋይ ሆኖአል።

*41፥10-12፤* በልበ ሙሉነት የቀረበ ጸሎት ነው።

41፥10 *የእጃቸውን እንድከፍላቸው፤* ንጉሥ እንደ መሆኑ መጠን ላደረሱበት በደል ብድራቸውን እንድከፍል ማለቱ ነው።

41፥12 *ይዘኸኛል ... ታኖረኛለህ፤ ታጽናኛለህ። በፊትህም፤* የእስራኤል ሰማያዊ ንጉሥ አገልጋይ በመሆን ማለት ነው (አባባሉ ፈሊጣዊ አነጋገር መሆኑን ለመመልከት 101፥7፤ 1ሳሙ16፥22፤ 1ነገ10፥8፤ 17፥11 ይመ)። *ለዘላለም፤* በእግዚአብሔር ፊት እንዳይኖር የሚያደርገው አንዳች ኀይል የለም (2ሳሙ7፥15-16 ይመ)።

*41፥13፤* ለአምልኮ የተሰበሰበው ሕዝብ 'በአንደኛ መጽሐፍ' ላይ ለተባሉት ነገሮች ምላሻቸውን እንዲሰጡ የሚጋብዝ ቃለ-ውዳሴ ነው (72፥18-19፤ 89፥52፤ 106፥48፤ 150 ይመ)።

*መዝሙር 42-43፤* ከአስጨናቂ ጠላቶች እጅ ለመዳንና (42፥9፤ 43፥2) በእግዚአብሔርም ቤተ መቅደስ ውስጥ ተመልሶ ለመኖር የቀረበ ጸሎት ነው፤ እነዚህ ሁለት መዝሙሮች (ምንም እንኳ በሰብዐ ሊቃናት ትርጕም እንደ ሁለት መዝሙር ሆነው ቢቀርቡም) በአንድ ትንፋሽ የተነገሩ መሆናቸውን ልዩ ከሆነው አወቃቀራቸውና ከሚያስተሳልፉትም ተመሳሳይ ፍሬ ሐሳብ መረዳት ይቻላል። መዝ 43 ከመዝ 42 እንዲለይ የተደረገው ለተለየ የቅዳሴ ሥርዐት ሲባል ሊሆን ይችላል (የመዝ9ን መግቢያ ይመ)። የዚህ መዝሙር ተናጋሪ ከቆሬ ወገን የሆነና በቤተ መቅደሱም ውስጥ የቅዳሴ አገልግሎት የሚሰጥ ሰው ሳይሆን አይቀርም (42፥4 እና የ42 ርእስ ማብ ይመ)። "እግዚአብሔርን የማይፈራ ሕዝብ" (43፥1) የተባሉት የመዝሙሩ ደራሲ ተማርኮ የሄደባቸው ሕዝቦች ሊሆኑ ይችላሉ (2ነገ12፥17-18 ይመ)። ይህ መዝሙር የመዝሙረኛው "ሁለተኛ መጽሐፍ" መጀመሪያ ሲሆን ይህ ሁለተኛ መጽሐፍ ከአንደኛው መጽሐፍ የሚለየው "ኤሎሂም" የሚለው የዕብራይስጥ ቃል በሁለተኛው መጽሐፍ ውስጥ በተደጋጋሚ መጠቀሱ ነው፤ በአንደኛው መጽሐፍ ውስጥ በተደጋጋሚ የተጠቀሰው ቃል "ያህዌ" የሚለው ነው። በአወቃቀር ረገድ ሲታይ የዚህ መዝሙር ሦስት አንጓዎች እኩኩል ሲሆኑ (እያንዳንዱ አንጓ አራት አራት ስንኞች አሉት) እያንዳንዱም አንጓ በተመሳሳይ አዝማቾች ተቀንብቦአል (42፥5:11፤ 43፥5)። በመካከል ላይ ያለው አንጓ ግን እያደገ የመጣውን ሐሳብ በማቋረጥ እግዚአብሔርን ስለመታመን ያወሳል። ከአዝማቾቹ በስተቀር ጸሎቱ የተቀነበበው የእግዚአብሔርን መገኘት በመናፈቅና (42፥1) በመሠዊያው ፊት እግዚአብሔርን ለማመስገን ቃል በመግባት ነው (43፥4)። የዚህ ዐይነት አዝማች አወቃቀር ያላቸውን መዝሙሮች ለማየት 46፤49፤59፤80፤107 ይመ።

42ርእስ *ለመዘምራን አለቃ፤* የመዝ 4 የርእስ ማብ ይመ። *የቆሬ ልጆች፤* ወይም "ለቆሬ ልጆች" ለኤዶታም የመዝ39 ርእስን ይመ። "የቆሬ ልጆች" የሚለው ሐረግ የሚያመለክተው ከቆሬ ወገን የሆኑትን ሌዋዊ መዘምራን ሲሆን በቅዳሴ ሥርዐት ላይ እንዲያገለግሉ የተሾሙት በዳዊት ነው። የቆሬ ወገኖች የሚወክሉት የሌዊን ልጅ የቆሐትን ቤተ ሰብ ነው። አሳፍ የጌርሶናውያን፣ ኤዶታም ደግሞ የመራሪ መዘምራን አለቃ እንደ ነበሩ ሁሉ፣ ኤማንም በዳዊት ዘመነ መንግሥት የቆሬ መዘምራን አለቃ ነበር (1ዜና6፥31-47 እንዲሁም የመዝ39 እና 88 ርእስን ይመ)። "በቆሬ ልጆች" ስም ከሚጠሩት ሰባት መዝሙሮች ውስጥ ይህ መዝሙር የመጀመሪያው ነው (42፥49)፤ ሌሎች አራት መዝሙሮች ደግሞ በሦስተኛው መጽሐፍ ውስጥ ይገኛሉ (መዝ 84-85፤ 87-88)።

*42፥1-4፤* በቤተ መቅደስ ውስጥ በእግዚአብሔር ፊት ለመሆን ያለውን ጕጕት ያመለክታል።

42፥1 *ዋላ የምንጭ ውሃ ለማግኘት እንደሚናፍቅ፤* ዋላ በተለይ አዳኞች በከበቡት ጊዜ ከምንጭ ውሃ ለመጠጣት እንደሚጓጓ ሁሉ መዝሙረኛውም አሳዳጆቹ ባየሉበት ጊዜ እግዚአብሔርን ለማየት ተጠምቶአል።

42፥2 *ሕያው አምላክን፤* ዘዳ5፥26 ይመ። *መቼ?* አሁን በቤተ መቅደስ ለመገኘት ሁኔታዎች አልፈቀዱለትም (ቍ9፤ 43፥1-2 ይመ)። *የማየው፤* ከእርሱ ጋር ኅብረት አደርጋለሁ ማለቱ ነው (ዘፀ19፥17፤ 29፥42-43፤ 30፥6:36 ይመ)።

42፥3 *አምላክህ የት አለ?* የ10፥11 ማብ ይመ። *ቀንና ሌሊት፤* ቍ8:10 ይመ።

42፥4 *ነፍሴ፤* የ6፥3 ማብ ይመ። *እየመራሁ፤* መዝሙረኛው በቤተ መቅደስ ውስጥ የመሪነት ሚና እንደ ነበረው ያመለክታል።

*42፥5፤* በእምነት ጸንቶ ስለመኖር የሚያሳስብ ነው

ተስፋሽን በእምላክ ላይ አድርጊ፤
  አዳኜና [6]አምላኬን፣
  ገና አመሰግነዋለሁና፡፡

ነፍሴ በውስጤ ተክዛለች፤
  ስለዚህ በዮርዳኖስ ምድር፣
በአርሞንኤም ከፍታ፣
  በሚዛር ተራራ አስብሃለሁ፡፡
[7]በፏፏቴህ ማስገምገም፣
  አንዱ ጥልቅ ሌላውን ጥልቅ ይጣራል፤
ማዕበልህና ሞገድህ ሁሉ፣
  ሙሉ በሙሉ አጥለቀለቀኝ፡፡

[8]እግዚአብሔር ምሕረቱን በቀን ያዝዛል፤
  ዝማሬውም በሌሊት በእኔ ዘንድ አለ፤
  ይህም ለሕይወቴ አምላክ የማቀርበው
    ጸሎት ነው፡፡

[9]እግዚአብሔር ዐለቴን፣
  "ለምን ረሳኸኝ?
ጠላትስ እያስጨነቀኝ፣
  ለምን በሐዘን እመላለሳለሁ?" እለዋለሁ፡፡
[10]ጠላቶቼ ቀኑን ሙሉ፣
  "አምላክህ የት አለ?" እያሉ፣
በነገር ጠዘጠዙኝ፣
  ዐጥንቴም ደቀቀ፡፡

[11]ነፍሴ ሆይ፤ ለምን ትተክዢያለሽ?
  ለምንስ በውስጤ ትታወኪያለሽ?
ተስፋሽን በእምላክ ላይ አድርጊ፣
  አዳኜና አምላኬን፣
  ገና አመሰግነዋለሁ፡፡

42፥6 ቍ11፤ዘፍ 13፥10፤ዘኍ13፥29፤ ዘዳ3፥8፤4፥48፤መዝ43፥5፤63፥6፤77፥11
42፥7 ዘፍ1፥2፤7፥11፤መዝ69፥2፤ዮና2፥3
42፥8 መዝ16፥7፤ 57፥3፤77፥6፤133፥3፤ መክ5፥18፤8፥15
42፥9 ኢዮ20፥19፤ መዝ9፥13፤10፥11፤18፥31፤35፥14፤43፥2፤ 106፥42
42፥10 ቍ3፤ዘዳ 32፥27፤መዝ6፥2፤44፥16፤89፥51፤102፥8፤ 119፥42
42፥11 ቍ5፤መዝ 43፥5
43፥1 መሳ6፥31፤ መዝ25፥20፤36፥3፤10 9፥2
43፥2 መዝ35፥14፤ 42፥9፤44፥9፤74፥1፤8 8፥14፤89፥38
43፥3 2ሳሙ15፥25፤መዝ2፥6፤25፥5፤26፥3፤27፥1
43፥4 ዘፍ4፥21፤ መዝ16፥3፤21፥6፤26፥6፤42፥2፤84፥3
43፥5 መዝ42፥6
44፥1 ዘጸ32፥7፤ መሳ6፥13፤2ሳሙ7፥22፤1ዜና17፥20፤ኢዮ 37፥23፤ኢር26፥11

## መዝሙር 43[a]

### በስደት ላይ ያለ ሌዋዊ ልቅሶ

[1]አምላክ ሆይ፤ ፍረድልኝ፤
  ከጽድቅ ከራቀ ሕዝብ ጋር ተሟገትልኝ፤
  ከአታላዮችና ከክፉዎች ሰዎችም አድነኝ፡፡
[2]አምላክ ሆይ፤ አንተ ብርታቴ ነህና፣
  ለምን ተውኸኝ?
ጠላትስ እያስጨነቀኝ፣
  ለምን በሐዘን እመላለሳለሁ?
[3]ብርሃንህንና እውነትህን ላክ፤
  እነርሱ ይምሩኝ፤
ወደ ተቀደሰው ተራራህ፣
  ወደ ማደሪያህ ያድርሱኝ፡፡

[4]እኔም ወደ እግዚአብሔር መሠዊያ እቀናለሁ፤
  ፍጹም ደስታዬ ወደ ሆነው አምላክ
    እሄዳለሁ፤
እግዚአብሔር አምላኬ ሆይ፣
  በበገና አመሰግንሃለሁ፡፡

[5]ነፍሴ ሆይ፤ ለምን ትተክዢያለሽ?
  ለምንስ በውስጤ ትታወኪያለሽ?
ተስፋሽን በእምላክ ላይ አድርጊ፤
  አዳኜና አምላኬን፣
  ገና አመሰግነዋለሁና፡፡

## መዝሙር 44

### ብሔራዊ ሰቆቃ

*ለመዘምራን አለቃ፤ የቆሬ ልጆች ትምህርት፡፡[b]*

[1]አምላክ ሆይ፤ በጆሮአችን ሰምተናል፤

[a]43 በብዙ የዕብራይስጥ ቅጆች መዝሙር42 እና 43 አንድ መዝሙር ነው፡፡
[b]44ርእስ የሥነ ጽሑፉን ትርጉ ወይም የመዝሙሩን ሁኔታ የሚያሳይ ሊሆን ይችላል፡፡

(27፥13-14 እና የመዝ27 መግቢያን ይመ)፡፡

*42፥6-10፤* ነፍሱ በእጅጉ የተጨነቀችበትን መንሥኤ ያመለክታል፡፡

42፥6 *አመሰግነዋለሁና፤* መድኅን ስለ ሆነኝ አመሰግነዋለሁ ማለቱ ነው (የ7፥17፤ 9፥1 ማብ 43፥4 ይመ)፡፡ *ነፍሴ ትተክዛለች፤* ቍ5:11፤ 43፥5 ይመ፡፡ *አስብሃለሁ፤* በስደት ላይ ሳለ ከእግዚአብሔር ጋር ሐሤት የሚያደርግበት ኅብረት እንደ ነበረው እንደሚያስታውስ ሁሉ (ቍ4) አሁንም በስደት ላይ እያለ እግዚአብሔርንና የደረሰበትንም ሥቃይ ያስታውሳል (ቍ7:9-10) ያም ሆኖ ግን ተስፋ ቢስ አይደለም (ቍ8)፡፡ *ምድር ... በሚዛር ተራራ፤* ምናልባት የመዝሙሩ ደራሲ ከእስራኤልና ከይሁዳ ውጪ በስደት ላይ እንዳለ ሊያመለክት ይችላል፡፡ በእግዚአብሔር ፊት ለመሆን የሚናፍቁና ልዩ መገለጡን የሚሹ ሁሉ የጓጉለትን ወዲያውኑ ላያገኙ ይችላሉ፤ ጠንካራ እምነት ያላቸው ግን አሁንም ከፊቱ አይርቁም፤ ልዩ መገለጡንም ተግተው ይፈልጋሉ፡፡ ጌታ ኢየሱስ ሙሉ በረከቱን የሚሰጠው እንዲሁ ተደላድለው ለተቀመጡት ክርስቲያኖች ሳይሆን ጽድቅን ለሚራቡና ለሚጠሙ መሆኑን እርሱ ራሱ ተናግሮአል (ማቴ5፥6)፡፡

42፥7 *በፏፏቴ ... አንዱ ጥልቅ፤* መዝሙረኛው የደረሰበትን ጽኑ መከራ ምስል ከሣች በሆነ መንገድ አንድ በአንድ ይገልጣል፤ በተከታዮቹም ጥቅሶች ላይ የመዝሙረኛው ጭንቀት ሥዕላዊ በሆነ መልክ ቀርቦአል (69፥1-2፤ 88፥7፤ ዮና 2፥3:5 እንዲሁም የ32፥6 ማብ ይመ)፡፡ በመዝሙረኛው ላይ እንዲህ ያሉ መዓቶች እንዲደርስ በማድረግ እግዚአብሔር በሥቃዩ ውስጥ ተሳትፎአል ማለት ይቻላል፡፡ ለመዝሙረኛው እግዚአብሔር "የረሳው" (ቍ9) ወይም "የተወው" (43፥2) ሊመስለው ይችላል፡፡ መዝሙረኛው ግን በዚህና በሕይወቱ ውስጥ ባለ ኀጢአት መካከል ምንም ዐይነት ተዛምዶ አላደረገም (መዝ44፡77 ይመ)፡፡

*42፥8፤* መከራ እንደ ጐርፍ ቢያጥለቀልቀውም አሁንም በአምላኩ እንደሚታመን ያረጋግጣል፡፡ እንዲህም ሲል "እግዚአብሔር ፍቅሩን በቀን ይልካል፣ ዝማሬውም በሌሊት አይለየኝም" ማለቱ ነው (ቍ3 እና የ3፥7 ማብ ይመ)፡፡ *እግዚአብሔር፤* በዚህ መዝሙር ውስጥ በዚህ ቦታ ብቻ ማለትም በመዝሙሩ እምብርት ላይ የሚገኝ ቃል ነው (መግቢያውን ይመ)፡፡ *ምሕረቱን ያዛል፤* አንድ መልእክተኛ ፈቃዱን ለማድረግ እንደሚሄድ ሁሉ እንዲሁ ምሕረቱን ይሰዳል (43፥3 ይመ)፡፡ *ምሕረቱን፤* የ6፥4 ማብ ይመ፡፡ *ዝማሬውም፤* ስለ ጌታ የሚያወሣ መዝሙር ነው፡፡ *ጸሎት፤* ምስጋናና ጸሎት በመዝሙረኛው ዘንድ አይነጣጠሉም፡፡

*42፥9፤* በመዝ43፥2 ላይ ይኸው ሐሳብ በድጋሚ ተንጸባርቆአል፡፡ *ዐለቴን፤* የ18፥2 ማብ ይመ፡፡ *ለምን ረሳኸኝ? ... ለምን?* የ6፥3 ማብ ይመ፡፡ (እንዲሁም ከመጽሐፉ መግቢያ "ትምህርተ-መለኮት" የሚለውን ይመ)፡፡

*42፥10፤* ቍ3 ይመ፡፡ *ዐጥንቴም፤* የ6፥2 ማብ ይመ፡፡

*43፥1-4፤* ከጠላት እጅ ለመዳንና በእግዚአብሔርም ፊት እንደ ገና ተመልሶ ለመቅረብ የቀረበ ልመና ነው፡፡

*43፥1፤* በፍርድ ቤት ቋንቋ የቀረበ ልመና ነው (የመዝ17 መግቢያን ይመ)፡፡

*43፥2፤* በ42፥9 ላይ የተጠቀሰውን ሐሳብ እንደ ገና መልሶ ያስተጋባል፡፡

43፥3 *ብርሃንህንና እውነትህን፤* የእግዚአብሔር መልእክተኛ በመሆን በሰውኛ አገላለጽ ቀርበዋል፤ እነርሱም የእግዚአብሔርን ማዳን እውን የሚያደርጉና (ብርሃን፤ የ27፥1 ማብ ይመ)፤ በእርሱም ስም ሆነው እንክብካቤውን እውን የሚያደርጉ ናቸው (እውነት፤ 26፥3፤ 30፥9፤ 40፥10 ይመ)፤ እነዚህ ወደ መቅደስህ ይምሩኝ ይላል መዝሙረኛው፡፡ *ወደ ተቀደሰውም ተራራህ፤* የ2፥6 ማብ ይመ፡፡

*43፥4፤* የ7፥17 ማብ ይመ፡፡ *መሠዊያ፤* 26፥6 እና ማብ ይመ፡፡

*መዝሙር 44፤* እስራኤላውያን ጠላት ከፍተኛ ሽንፈት ካደረሰባቸው በኋላ በሥቃይ ውስጥ ሆነው ያቀረቡት ልመና ነው፡፡ ከቍ17-22 ያለውን ሐሳብ መሠረት በማድረግ ብቻ ይህንን መዝሙር እስራኤል ከእግዚአብሔር ጋር ለገባችው ቃል ኪዳን ታማኝ ካልሆነች በጠላት እጅ ከፍተኛ ሽንፈት ካደረሰባቸው ከሚለው ከነቢያት ትንቢት ጋር ማዛመድ አስቸጋሪ ነው፡፡ መዝሙሩ

አባቶቻችን በቀድሞ ዘመን፣
እነርሱ በነበሩበት ዘመን፣
ያደረግኸውን ነግረውናል።
2ሕዝቦችን በእጅህ አሳደህ አወጣሃቸው፤
አባቶቻችንን ግን ተክልሃቸው፤
ሕዝቦችን አደቀቅህ፤
አባቶቻችንን ግን ነጻ አወጣሃቸው።
3ምድሪቱን የወረሱት በሰይፋቸው
አልነበረም፤
ድልንም የተጐናጸፉት በክንዳቸው
አይደለም፤
አንተ ወደሃቸዋልና ቀኝ እጅህ፣
ክንድህና የፊትህ ብርሃን ይህን አደረገ።

4እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ ንጉሤ ነህ፤ሖ
ያዕቆብም ድል እንዲያደርግ የወሰንህ
አንተ ነህ።
5በአንተ ጠላቶቻችን በመጡበት እንዲ
መለሱ እናደርጋለን፤
በስምህም ባላጋራዎቻችንን ከእግራችን
በታች እንረግጣለን።
6በቀስቴ አልተማመንም፤
ሰይፌም አያስጥለኝም።
7አንተ ግን በጠላቶቻችን ላይ ድልን
ትሰጠናለህ፤
ባላንጣዎቻችንንም ታሳፍራለህ።

8ዘወትር በእግዚአብሔር እንመካለን፤
ስምህንም ለዘላለም እንወድሳለን። ሴላ

9አሁን ግን እነሆ ትተኸናል፤
አሳፍረኸናልም፤
ከሰራዊታችንም ጋር አትወጣም።

44፥2 ዘፀ15፥17፤ ኢሱ3፥10፤መሳ4፥23፤ 2ዜና14፥13፤መዝ80፥9፤ኢሳ60፥21፤ኤር 32፥23፤ሐሥ7፥45 44፥3 ዘፀ15፥16፤ዘዳ 4፥37፤ኢሱ24፥12፤ መዝ77፥15፤78፥54፤ 79፥11፤89፥10፡15፤ 98፥1፤ኢሳ40፥10፤ 52፥10፤63፥5 44፥4 መዝ5፥2፤21፥ 5፤24፥7 44፥5 ኢሱ23፥5፤ መዝ60፥12፤108፥13 44፥6 ዘፍ48፥22፤ ሆሴ1፥7 44፥7 ዘዳ20፥4፤ኢዮ 8፥22 44፥8 መዝ30፥12፤ 34፥2፤52፥1፤1ቆሮ 1፥31፤2ቆሮ10፥17 44፥9 ዘዳ8፥3፤ 31፥17፤ኢሱ7፥12፤ መዝ43፥2፤107፥39፤ 108፥11፤ኢሳ5፥15 44፥10 ዘሌ26፥17 ፤መሳ2፥14 44፥11 ቍ22፤ዘሌ 26፥33፤መዝ9፥11፤ ኤር12፥3፤ሕዝ6፥8፤ ዘካ2፥6 44፥12 ዘዳ32፥30፤ ኢሳ50፥1፤52፥3፤ኤር 15፥13 44፥13 ዘዳ28፥37፤ 2ዜና29፥8፤መዝ79፥4 ፤80፥6፤89፥41፤ኢሳ 30፥3፤ኤር25፥9፤42፥ 18፤44፥8፤ሕዝ23፥32 ፤ሚክ2፥6 44፥14 1ነገ9፥7፤

10ከጠላት ፊት እንድናፈገፍግ አደረግኸን፤
ባላንጣዎቻችንም ዘረፉን።
11እንደሚታረዱ በጎች አደረግኸን፤
በሕዝቦችም መካከል በተንኸን።
12ሕዝብህን በርካሽ ዋጋ ሸጥኸው፤
ከሽያጩም ያገኘኸው ትርፍ የለም።
13ለጎረቤቶቻችን ስድብ፣
በዙሪያችን ላሉትም መሣቂያና መዘበቻ
አደረግኸን።
14በሕዝቦች ዘንድ መተረቻ፣
በሰዎች መካከል በንቀት ራስ መነቅነቂያ
አደረግኸን።
15ውርደቴ ቀኑን ሙሉ በፊቴ ነው፤
ፊቴም ዕፍረትን ተከናንቦአል።
16ይህም ከሚዘልፍና ከሚያላግጥ ሰው
ድምፅ የተነሣ፣
ከጠላትና ከተበቃይ ሁኔታ የተነሣ ነው።

17አንተን ሳንረሳ፣
ለኪዳንህም ታማኝነታችንን ሳናጓድል፣
ይህ ሁሉ ደረሰብን።
18ልባችን ወደ ኋላ አላለም፤
እግራችንም ከመንገድህ አልወጣም።
19አንተ ግን ተኰላዎች በሚውሉበት ቦታ
ሰባብረህ ጣልኸን፤

2ነገ19፥21 44፥15 ዘፍ30፥23፤ 2ዜና32፥21፤መዝ34፥5፤35፥26 44፥16 1ሳሙ18፥25፤መዝ10፥13፤42፥10፤55፥3፤74፥10፤ኤር11፥19 ፤ሮሜ12፥19 44፥17 ዘዳ6፥12፤32፥18፤መዝ119፥16፡61፡153፡ 176፤ምሳ3፥1 44፥18 መዝ119፥ 51፡157 44፥19 2ዜና14፥13 ፤ኢዮ3፥5፤30፥29፤ መዝ51፥8፤ኢሳ34፥13

ሖ4 የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም የሱርስቱ ቅጅ *ንጉሤ ነህ፤ አምላኬም ነህ* ይላሉ፤ ዕብራይስጡ ደግሞ፣ *ንጉሤ እግዚአብሔር ሆይ፤* ይላል።

ምናልባት የይሁዳን መንግሥት ተመክሮ ሳያጣቅስ (ሳያመለክት) አይቀርም (ይሁዳ እስከ 586 ዓ.ቅ.ክ ድረስ በመንግሥትነት ቈይታለች)፤ ይህም ምናልባት በኢዮሣፍጥ ወይም በሕዝቅያስ ዘመነ መንግሥት ሊሆን ይችላል። ባወቃቀር ረገድ ሲታይ የመዝ ሙሩ ዐቢይ ሐሳብ አንዱ በሌላው ላይ እየተነባበረ እስከ መጨረ ሻው ቍጥር ድረስ ይዘልቃል። የመዝሙሩ አወቃቀር የጥንት አሶራውያንና በባቢሎናውያን ለቤተ መቅደሶቻቸው የሚሰሩትን ጒልላት ይመስላል። አሶራውያንና ባቢሎናዉያን ለቤተ መቅደሶቻ ቸው የሚሰሩት ጒልላት እንደ ፒራሚድ ያለ ወይም እንደ ተራራ ያለ ቅርጽ ነው ያለው (ዘፍ11፥4 እና ማብ ይመ)። በመዝሙሩ ውስጥ በመጀመሪያ የምናገኘው እግዚአብሔር ከዚህ ቀደም ስለሰ ጣቸው ድል የቀረበ ምስጋና (ቍ1-8) ሲሆን በሁለተኛው ደረጃ የምናገኘው ደግሞ ከዚህ በፊት ስለደረሰባቸው ሽንፈትና ስላስከተ ለውም ጣስ ነው (ቍ9-16)፤ በሦስተኛ ደረጃ ንጹሕ መሆናቸውን የሚገልጽ አቤቱታ የቀረበ ሲሆን (ቍ17-22) በመጨረሻም ጸሎት (ምልጃ) ቀርቦአል (ቍ23-24)። አንዱ ባንዱ ላይ እየተነባ በረ የቀረበው ዐቢይ ሐሳብ (ቀድሞ የተደረገላቸውን ምሕረት የሚያስታውስ፣ አሁን ያሉበትን መከራ የሚያወሳውና ለገቡት ቃል ኪዳን ታማኝ መሆናቸውን የሚገልጸው) ሁሉም በየራሱ የሚያቀርበው የርዳታ ጥሪ አለ (መዝ40 እና መግቢያውን እንዲ ሁም በመዝ40፤ 89 ላይ የቀረበውን መቅድም ይመ)።

*44ርእስ፤* የመዝ 42 የርእስ ማብ ይመ።

*44፥1-8፤* እግዚአብሔር ከዚህ ቀደም ስለ ሰጣቸው ድል የቀረበ ምስጋና ነው፤ ድሎችም (1) እስራኤል በተስፋዪቱ ምድር ላይ መተከሏንና (ቍ1-3)፤ (2) በተስፋዪቱም ምድር ያለሥጋት ተደላድላ መቀመጧን የሚያወሱ ናቸው (ቍ4-8)።

*44፥1፤* 78፥3 ይመ።

44፥3 *የፊትህ ብርሃን፤* የ4፥6 እና የ13፥1 ማብ ይመ።

44፥4 *ንጉሤ (የእኔ)፤* በዚህ ቦታና በዚህ መዝሙር ውስጥ በአንደኛ መደብ ነጠላ ቍጥር የተነገረው ተውላጠ ስም የሚ ወክለው መላውን ሕዝብ ነው፤ የመዝ 30 የርእስ ማብ ይመ። *ያዕቆብ፤* የ14፥7 ማብ ይመ።

44፥5፡8 *በስምህም፤* ቍ20፤ እንዲሁም የ5፥11 ማብ ይመ።

*44፥9-16፤* አሁን ግን ትተኸናል፤ (1) ሽንፈትን እንድን ቀምስ አድርገኸናል (ቍ9-12)፤ (2) በጠላቶቻችንም ፊት እንድና ፍር አድርገኸናል (ቍ13-16 ይመ) ማለት ነው።

44፥9 *ትተኸናል፤* እንደ መዝሙረኛው አስተያየት የእግዚ አብሔር ሕዝብ ሥቃይና ሽንፈት የደረሰባቸው እግዚአብሔር ስለ ተዋቸው ነው (ቍ9-16)፤ መዝሙረኛው ግን በሁኔታው ግራ የተጋባ ይመስላል፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር የተዋቸው የገቡ ትን ቃል ኪዳን ሳያፈርሱ ነው (ቍ17-19)። ከዚህ ላይ መዝሙ ረኛው የሚያንጸባርቀው የእግዚአብሔርን ልጆች ተመክሮ ነው፤ እንደ ኢዮብ ምንም ነቀፋ የሌለባቸው ሰዎች፣ የእግዚአብሔር ጥበቃ ሊለያቸው፣ በመከራ፣ በጨለማና በፈተና ሕይወት ውስጥ ሊያልፉ ይችላሉ፤ ይህ ዐይነቱ ገጠመኝ ምን እንደ ሚመስልም በቍ22 ላይ ተመልክቶአል።

44፥11 *እንደሚታረዱ በጎች አደረግኸን፤* እረኛና ንጉሣ ችን የሆንኸውን ያህል ከጠላት እጅ አላዳንከንም ማለቱ ነው (ቍ4 እና፤ የ23፥1 ማብ ይመ)።

44፥12 *ሕዝብህን ... ሸጥኸው፤* ዋጋ እንደሌለው ንብረት ቈጠርከን ማለቱ ነው (ዘፀ32፥30፤ መሳ2፥14 ይመ)፤ *በርካሽ ዋጋ፤* ፋይዳ ቢስ አደረግኸን ማለቱ ነው (ኢሳ52፥3፤ ኤር15፥13 ይመ፤ ከኢሳ43፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ)።

44፥14 *ራሳቸውን ይነቀንቁብናል፤* ያላግጡብናል ማለቱ ነው (64፥8 ይመ)።

44፥16 *ሊበቀለኝ በሚሻ ጠላት፤* 8፥2 እና ማብ ይመ።

*44፥17-22፤* ለአንተ ያለንን ታማኝነት አላጓደልንም፤ (1) ለቃል ኪዳንህ ያለን አክብሮትም ከቶ አልተለወጠም (ቍ17-19)፤ (2) ወደ ባእዳን አማልክትም እንዳልሄድን አንተ ራስህ ታውቃለህ (ቍ20-22)።

44፥17 *ለኪዳንህም፤* ዘፀ19-24 ይመ።

44፥18 *ልባችን፤* የ4፥7 ማብ ይመ። *ከመንገድህ፤* በእግዚ አብሔር ቃል ኪዳን ላይ ቍልጭ ብሎ ከተመለከተው መንገድ ማለት ነው (የ5፥8 ማብ ይመ)።

44፥19 *ተኰላዎች በሚውሉበት፤* ሰው የማይኖርበት ጠፍ ቦታ ማለት ነው። *አንተ ግን ሰባብረህ ጣልኸን፤* ይህ ግን ለቃል

[14]ሰው በሀብቱ ብዛት ደስ እንደሚለው፣
 ምስክርነትህን በመከተል ደስ ይለኛል።
[15]ድንጋጌህን አሰላስላለሁ፤
 ልቤን በመንገድህ ላይ ጥያለሁ።
[16]በሥርዐትህ ደስ ይለኛል፤
 ቃልህንም አልዘነጋም።

ג ጋሜል

[17]ሕያው እንድሆን፣ ቃልህንም እንድጠብቅ፣
 ለአገልጋይህ መልካም አድርግ።
[18]ከሕግህ ድንቅ ነገርን እንዳይ፣
 ዐይኖቼን ክፈት።
[19]እኔ በምድር ላይ መጻተኛ ነኝ፤
 ትእዛዛትህን ከእኔ አትሰውር።
[20]ዘወትር ደንብህን በመናፈቅ፣
 ነፍሴ እጅግ ዛለች።
[21]ከትእዛዛትህ የሳቱትን፣
 እብሪተኞችንና ርጉሞችን ትገሥጻለህ።
[22]ምስክርነትህን ጠብቄአለሁና፣
 ስድብንና ንቀትን ከእኔ አርቅ።
[23]ገዦች ተቀምጠው ቢዶልቱብኝ እንኳ፣
 አገልጋይህ ሥርዐትህን ያሰላስላል።
[24]ምስክርነትህ ለእኔ ደስታዬ ነው፤
 መካሪዬም ነው።

ד ዳሌጥ

[25]ነፍሴ ከዐፈር ጋር ተጣበቀች፤
 እንደ ቃልህ መልሰህ ሕያው አድርገኝ።
[26]ስለ መንገዴ ገልጬ ነገርሁህ፤ አንተም
 መለስህልኝ፤
 ሥርዐትህን አስተምረኝ።
[27]የድንጋጌህን መንገድ እንዳስተውል
 አድርገኝ፤
 እኔም ድንቅ ሥራህን አሰላስላለሁ።
[28]ነፍሴ በሐዘን ተዝለፈለፈች፤
 እንደ ቃልህ አበርታኝ።
[29]የሽንገላን መንገድ ከእኔ አርቅ፤
 ሕግህን በጸጋህ ስጠኝ።
[30]የእውነትን መንገድ መርጫለሁ፤
 ሕግህንም ፊት ለፊቴ አድርጌአለሁ።
[31]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከምስክርነትህ ጋር
 ተጣብቄአለሁ፤
 አሳልፈህ ለውርደት አትስጠኝ።
[32]ልቤን አስፍተህልኛልና፣
 በትእዛዛትህ መንገድ እሮጣለሁ።

ה ሄ

[33]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ የሥርዐትህን መንገድ
 አስተምረኝ፤
 እኔም እስከ መጨረሻው እጠብቀዋለሁ።
[34]ሕግህን እንድጠብቅ፣ በፍጹም ልቤም
 እንድታዘዘው፣
 ማስተዋልን ስጠኝ።
[35]በእርሷ ደስ ይለኛልና፣

119፥14 ቍ111
119፥15 ቍ97፡ 148፤መዝ1፥2
119፥16መዝ112፥1
119፥17ቍ67፤መዝ 13፥6፤103፥20፤ 116፥7
119፥19 ዘፍ23፥4፤ ዕብ11፥13
119፥20 ቍ131፤ መዝ42፥2፤63፥1፤ 84፥2፤ኢሳ26፥9
119፥21 ቍ10፡51 ፤ዘዳ27፥26፤ኢዮ30፥1 ፤መዝ5፥5፤ኤር20፥7 ፤50፥32፤ዳን4፥37፤ ሚል3፥15
119፥22 ቍ2፤መዝ 39፥8
119፥25 ቍ9፡50፡ 107፤መዝ44፥25፤ 143፥11
119፥26 መዝ25፥4 ፤27፥11፤86፥11
119፥27መዝ105፥2 ፤145፥5
119፥28 ቍ9፤መዝ 6፥7፤18፥1፤116፥3፤ ኢሳ40፥29፤41፥10፤ 51፥11፤ኤር45፥3
119፥29 ዘኍ6፥25፤ መዝ26፥4
119፥30 ኢሱ24፥22 ፤መዝ26፥3፤108፥1
119፥31 ዘዳ10፥20
119፥33 ቍ12
119፥34 ቍ27፡69፡73፡144፡169፤ዘዳ6፥25፤ኢዮ32፥8፤ምሳ2፥6፤ ዳን2፥21፤ያዕ1፥5 119፥35 ቍ32፤መዝ1፥2፤25፥4-5

119፥14 *ሰው በሀብቱ ... ደስ እንደሚለው፤* ቍ72፡ 111፡162 ይመ።

119፥15 *በመንገድህ፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ ቍ3 ላይ መንገዶችህ ከሚለው ጋር ተመሳሳይ ነው (እነዚህ ሁለት የዕብራይስጥ ቃላት በ25፥4 ላይ፣ ፊት ለፊት ወይም ጐን ለጐን ተነጻጽረው ቀርበዋል)።

*119፥17-24፤* ለእግዚአብሔር ሕግ የሚታዘዙ የእግዚአብሔር አገልጋይ መሆናቸውን ያሳያል፤ ይህም ከዓለም እብሪተኞች ጋር አንድነት የሌላቸው መሆኑን ያረጋግጣል (ቍ21)።

119፥17 *ቃልህንም እንድጠብቅ፤* ከእግዚአብሔር ጥበቃና በረከት የተነሣ፣ የእርሱን ቃል እታዘዛለሁ ማለቱ ነው።

119፥18 *ድንቅ ነገርን፤* ይህ ሐረግ አብዛኛውን ጊዜ የሚያመለክተው የእግዚአብሔርን የማዳን ሥራ ነው (9፥1 እና ማብ ይመ)፤ ይሁን እንጂ የእግዚአብሔርም ሕግ ራሱ ድንቅ ነገሮችን በውስጡ ይዞአል (ቍ27 ይመ)።

119፥19 *እኔ በምድር ላይ መጻተኛ ነኝ፤* የእግዚአብሔር አገልጋይ ማለትም የመንግሥቱ ወራሽ በመሆኑ፣ የትኛውም ምድራዊ መንግሥት ዜጋ አይደለም (39፥12እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም የቍ54 ማብ ይመ)።

119፥20 *ነፍሴ ...፤* እኔ ራሴ ማለት ነው (ቍ28፡81 ይመ። እንዲሁም የ6፥3 ማብ ይመ)።

119፥21 *እብሪተኞችንና፤* የራሳቸው ሕግ እነርሱ ራሳቸው መሆናቸውን የሚናገሩ ሲሆን እንዲሁም በ10፥2-11 ላይ በዝርዝር ተነግሮአል (ቍ51፡69፡78፡85፡122 ይመ፤ እንዲሁም የ31፥23 ማብ ይመ)። የሚቀጥሉት ሁለት ቍጥሮችና ሌሎችም በርካታ ቍጥሮች እንደሚያሳዩት መዝሙረኛው ለእግዚአብሔርና ለሕጉም ካለው ቅናት የተነሣ በጠላቶቹ እጅ አያሌ መከራን ተቀብሎአል። *ርጉሞችን፤* የእግዚአብሔር ፍርድ በላያቸው ሊገለጥ የተቃረቡ ማለት ነው።

119፥22 *ስድብንና ንቀትን፤* በእብሪተኞች ማለት ነው።

119፥23 *ገዦች፤* መዝሙረኛው "በነገሥታት ፊት" (ቍ46) የሚል ነገር በመናገሩና "ገዦች" የሚያሳድዱት (ቍ161) መሆኑን በመግለጹ የኀላፊነት ቦታ የተሰጠው ካህን ሳይሆን አይቀርም (ከካህንም ተግባሮች አንዱ የእግዚአብሔርን ሕግ ማስተማር እንደ ነበር ይታወቃል፤ ዘሌ10፥11፤ ዕዝ7፥6፤ ነህ8፥2-8፤ ኤር 2፥8፤ 18፥18፤ ሚል2፥7 ይመ። እንዲሁም የቍ57 ማብ ይመ)። (እነዚህ ነገሥታትና ገዦች ምናልባት ከነገሥታቱ ዘመን ጀምሮ የነበሩ የእስራኤል ነገሥታት ወይም ከምርኮ በኋላ የነበሩ የፋርስ ነገሥታት ሳይሆኑ አይቀሩም)። *ተቀምጠው፤* በዚህች ዓለም ተደላድለው እንደ ተቀመጡ ማለት ነው፤ ይህ ግን መጻተኞችን አይመለከትም (ከቍ19 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቢዶልቱብኝም፤* ዓለማዊ አስተሳሰባቸ ውን በጋራ በሚመካከሩበት ሰዓት ከእነርሱ ጋር በሐሳብ የማይተባበረውን ያንቋሽሹታል፤ ያናንቁታልም፤ ይህም የሚሆንበት ምክንያት እርሱ በእግዚአብሔር ሥርዐቶች ደስ ስለ ሚሰኝና እነዚህንም ሥርዐቶች መካሮቹ ስላደረጋቸው ነው (ቍ24)።

*119፥25-32፤* "ዝቅ ዝቅ ብል" (ቍ25) ወይም "ነጻ ብወጣ" (ቍ32) የእግዚአብሔርን ቃል የሙጥኝ ለማለት ወስኖ አል (ቍ31)።

119፥25 *ወድቄአለሁ፤* መዝሙረኛው ስለደረሰበት ሐዘን፣ መከራና ሥቃይ ብዙ ይናገራል (ቍ28፡50፡67፡71፡75፡83፡92፡107፡ 143፡153፡ ይመ) የእግዚአብሔርን ቃል (ሕጉንና ተስፋውን ማለት ነው) የሕይወቱ ተስፋ በማድረጉ ጠላቶቹ ሲያንቋሽሹት፣ ሲያሙትና ሲያሳድዱት ይታያል (42፡51፡65፡69፡78፡85፡95፡110፡134፡ 141፡150፡154፡157፡161 ይመ። እንዲሁም የቍ6፤ 5፥9፤ 31፥11-12 ማብ ይመ)። *ከዐፈር፤* 44፥25 እና ማብ ይመ። *ቃልህ፤* በተለይ ተስፋውን ማለት ነው፤ ይህም በቍ28፡37፡42፡49፡65፡74፡81፡ 107፡114፡147፡ እንደ ተጻፈው ማለት ነው።

119፥27 *ድንቅ ሥራዎችህን፤* የቍ18 ማብ ይመ።

119፥29 *የሽንገላን መንገድ፤* ትክክልና ቀና መስሎ የሚታይ፣ ነገር ግን ወደ ሞት የሚመራ መንገድ ነው (ምሳ14፥12 ይመ)፤ ይህም መንገድ ታማኝ ከሆነውና (ቍ86፡138 ይመ) እውነትም ከሆነው (ቍ142፡151፡160 ይመ) ከእግዚአብሔር ሕግ ጋር ተቃራኒነው። *ሕግህን፤* ለትእዛዝህ ራሴን በታማኝነት ያስገዛሁ በመሆኔ በረከትህን እንዳገኝ ርዳኝ።

119፥30 *የእውነትን መንገድ፤* የቍ29 ማብ ይመ።

119፥31 *አሳልፈህ ... አትስጠኝ፤* የቍ6 ማብ ይመ።

119፥32 *ልቤን አስፍተህልኛልና፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ልቤን ነጻ አድርገኸዋልና" ማለት ነው፤ ይህም በደስታ አስፋኸው ማለት ነው (ኢሳ60፥5 "በደስታ ያብጣል" ይመ)። ሌሎች ደግሞ "ማስተዋልን ጨመርኽልኝ" በማለት ተርጕመውታል (1ነገ 4፥29፣ "የማስተዋል ብዛት/ስፋት")። *ልቤን፤* የ4፥7 ማብ ይመ።

*119፥33-40፤* ሥርዐቱን በሚናፍቅበት ጊዜ እግዚአብሔር ፈቃዱን እንዲያስታውቀው ያቀረበው ጸሎት ነው።

119፥34 ... *ልቤም፤* ቍ36 ይመ፤ እንዲሁም የ4፥7 ማብ ይመ።

በትእዛዝህ መንገድ ምራኝ።
36ከራስ ጥቅም ይልቅ፣
ልቤን ወደ ምስክርነትህ አዘንብል።
37ከንቱ ነገር ከማየት ዐይኖቼን መልስ፤
በራስህ መንገድ* እንደ ገና ሕያው
አድርገኝ።
38ትፈራ ዘንድ፣
ለአገልጋይህ የገባኸውን ቃል ፈጽም።
39የምፈራውን መዋረድ ከእኔ አርቅ፤
ደንብህ መልካም ነውና።
40እነሆ፤ ድንጋጌህን ናፈቅሁ፤
በጽድቅህ ሕያው አድርገኝ።

*ነ ዋው*

41*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ምሕረትህ ወደ እኔ
ይምጣ፤
ማዳንህም እንደ ቃልህ ይላክልኝ።
42በቃልህ ታምኛለሁና፣
ለሚሰድቡኝ መልስ እሰጣለሁ።
43ሕግህን ተስፋ አድርጌአለሁና፣
የእውነትን ቃል ከአፌ ፈጽመህ አታርቅ።
44ከዘላለም እስከ ዘላለም፣
ሕግህን ዘወትር እጠብቃለሁ።
45ሥርዐትህን እሻለሁና፣
እንደ ልቤ ወዲያ ወዲህ እመላለሳለሁ።
46ምስክርነትህን በነገሥታት ፊት እናገራለሁ፤
ይህን በማድረግም ዕፍረት አይሰማኝም።
47እኔ እወደዋለሁና፣
በትእዛዝህ ደስ ይለኛል።
48እጆቼን ወደምወዳቸው° ትእዛዛትህ
እነሣለሁ፤
ሥርዐትህንም አሰላስላለሁ።

*የ ዛይ*

49ለአገልጋይህ የገባኸውን ቃል አስብ፤
በዚያ ተስፋ ሰጥተኸኛልና።
50ቃልህ ሕያው ያደርገኛልና፣
ይህች በመከራዬ መጽናኛዬ ናት።
51እብሪተኞች እጅግ ተሣለቁብኝ፤
እኔ ግን ከሕግህ ንቅንቅ አላልሁም።
52*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከጥንት የነበረውን
ድንጋጌህን አሰብሁ፤
በዚህም ተጽናናሁ።
53ሕግህን ከተዉ ክፉዎች የተነሣ፣
ቍጣ ወረረኝ።
54በእንግድነቴ አገር፣
ሥርዐትህ መዝሙሬ ናት።
55*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ስምህን በሌሊት
አስባለሁ፤
ሕግህንም እጠብቃለሁ።
56ሥርዐትህን እከተላለሁ፤
ይህችም ተግባሬ ሆነች።

*ሀ ሔት*

57*እግዚአብሔር* ዕድል ፈንታዬ ነው፤
ቃልህን ለመታዘዝ ቈርጫለሁ።
58በፍጹም ልቤ ፊትህን ፈለግሁ፤
እንደ ቃልህ ቸርነትህን አሳየኝ።
59መንገዴን ቃኘሁ፤
አካሄዴንም ወደ ምስክርህ አቀናሁ።
60ትእዛዝህን ለመጠበቅ፣
ቸኰልሁ፤ አልዘገየሁም።
61የክፉዎች ገመድ ተተበተበብኝ፤
እኔ ግን ሕግህን አልረሳሁም።

119፥36 ኢሱ24፥23፤ሕዝ33፥31
119፥37 ቍ9:25፤መዝ71፥20
119፥38 ዘኍ23፥19
119፥39 ቍ22፤መዝ69፥9፤89፥51፤ኢሳ25፥8፤51፥7፤54፥4
119፥40 ቍ20:25:149:154
119፥41 ቍ76:116:154:170፤መዝ6፥4
119፥42 መዝ42፥10፤ምሳ27፥11
119፥43 ቍ74:81:114:147፤1ነገ17፥24
119፥44 ቍ33:34:55፤ዘዳ6፥25
115፥45 ቍ94:155
119፥46 ቍ6፤ማቴ10፥18፤ሐሥ26፥1-2
119፥47 ቍ77:97:127:143:159:163:165፤መዝ112፥1
119፥48 ዘፍ24፥63
119፥49 ቍ9:43
119፥50 ቍ25
119፥51 ቍ21፤ኢዮ 16፥10፤17፥2፤23፥11
119፥52 መዝ103፥18
119፥53 ዘፀ32፥19፤33፥4፤መዝ89፥30
119፥54 ቍ172፤መዝ101፥1፤138፥5
119፥55 ቍ44:62:72፤መዝ1፥2፤42፥8፤63፥6፤77፥2፤ኢሳ26፥9፤ሐሥ16፥25
119፥56 ቍ4:100:134:168፤ዘኍ15፥40
119፥57 ቍ17:67:101፤ዘዳ32፥9፤ኤር51፥19፤ሰቆ3፥24
119፥58 ቍ41፤ዘፍ 43፥29፤ዘዳ4፥29፤1ዜና16፥11፤ዕዝ9፥8፤መዝ34፥4 119፥59 ኢሱ24፥14-15፤መዝ39፥1 119፥60 ቍ115
119፥61 ቍ83: 109:153:176

*37 አንዳንድ ትርጕሞች *እንደ ቃልህ* ይላሉ።
°48 ወይም *ለምወዳቸው*

119፥36-37 *ልቤን ... ዐይኖቼ፤* 101፥2ለ-3ሀ እና ማብ ይመ።

119፥38 *ትፈራ ዘንድ፤* በሰጠው ተስፋ መሠረት የማዳን ሥራውን በመፈጸሙ እርሱ እውነተኛ አምላክ መሆኑን አረጋግጦ አል (130፥4፤ 2ሳሙ 7፥25-26፤ 1ነገ 8፥39-40፤ ኤር 33፥8-9 ይመ)።

119፥39 *የምፈራውን መዋረድ፤* የቍ6:25 ማብ ይመ።

119፥40 *በጽድቅህ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

*119፥41-48፤* እግዚአብሔር ይታደገኝ እውነቱንም ከአንደ በቴ አይውሰድብኝ፤ እኔም ሕጉን በሕይወቴ ዘመን ሁሉ አከብራ ለሁ፤ በነገሥታት ፊት ሕጉን እናገራለሁ፤ ምክንያቱም ትእዛዛቱን አፈቅራለሁና።

119፥41 *ምሕረትህ፤* ቍ64:76:88:124:149:159 ይመ። እንዲሁም የ6፥4 ማብ ይመ።

119፥42 *ለሚሰድቡኝ፤* የቍ25 ማብ ይመ ("ወድቄ አለሁ")። *በቃልህ፤* የቍ25 ማብ ይመ።

119፥43 *የእውነትን ቃል ከአፌ፤* ቍ13 እና ማብ ይመ። እንዲ ሁም ቍ46 ይመ።

119፥45 *እንደ ልቤ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ሰፊ ቦታ" ማለት ነው፤ ይህም ማለት በጭንቅና በመከራ ያልተከበበ ማለት ነው (18፥19 እና ማብ ይመ)።

119፥46 *በነገሥታት ፊት፤* እንግዲህ የባለመዝሙሩ ድፍ ረት እስከዚህ ድረስ ነው (የቍ23 ማብ ይመ)።

119፥48 *እጆቼን ወደ ... እነሣለሁ፤* ምስጋናን የሚያጅብ ድርጊት ነው (በ63፥4፤ በ134፥2 ላይ እንደ ተመለከተው ማለት ነው)፤ ስለዚህ ድርጊቱ "አመሰግንሃለሁ" ማለት ነው።

*119፥49-56፤* በምንም ዐይነት ሁኔታ ውስጥ ብሆን የእግዚ አብሔር ቃል መጽናኛዬና መመሪያዬ ነው።

*119፥49፤* ቃል የቍ25 ማብ ይመ።

119፥50-51 *ከመከራዬ ... እብሪተኞች ... ተሳለቁብኝ፤* የቍ25 ማብ ይመ ("ወደቅሁ")።

119፥51 *እብሪተኞች፤* የቍ21 ማብ ይመ።

119፥52 *ከጥንት፤* የእግዚአብሔር ሕግ የሚፍረከረክ አይደ ለም፤ ነገር ግን ከቶ በማይለወጠው ሥነ ምግባራዊ ባሕርያት ላይ ጸንቶ የተመሠረተ ነው። እንግዲህ ለመዝሙረኛው የመጽና ኛና ሕጉንም ከልብ ለመውደድ ምክንያት የሆነው ይህ ነው (ቍ89:144:152: 160 ይመ)።

119፥53 *ቍጣ ወረረኝ፤* ለእግዚአብሔር ሕግ ያለው መንፈሳዊ ቅናት (ቍ136:139 ይመ) ሕጉን በሚቃወሙት ሰዎች ላይ (ቍ113:115:158 ተመ)፣ ጽድቅን የተሞላ ቍጣ ይቀሰቅስ ባቸዋል፤ ደግሞም ሕጉን በሚቃወሙ ሰዎች ላይ ጥላቻን ያመጣ ባቸዋል (ቍ104:128:163 ይመ)፤ የሚያከብሩትን ግን ወደ ራሱ ይስባቸዋል (ቍ63 ይመ)።

119፥54 *በእንግድነቴ አገር፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "በጊ ዜያዊ መጠለያዬ" ማለት ነው። የዚህ ቍጥር ሐሳብ ከቍ19 ጋር ተመሳሳይነት አለው (ማብ ይመ)።

119፥55 *ስምህን፤* የ5፥11 ማብ ይመ።

*119፥57-64፤* እግዚአብሔር የመዝሙረኛው እውነተኛ ዕድል ፈንታ ነው፤ ምክንያቱም ሕይወት በምድር ላይ ዋስትና ያላትና ደስተኛም ትሆን ዘንድ የሚያደርጋት የእግዚአብሔር ሕግ ነው። ስለዚህ የእግዚአብሔር ቃል ኪዳን ተስፋው ናቸው፤ እንዲሁም የእግዚአብሔር ጻድቅ ሕጎች ደስታው ናቸው።

119፥57 *ዕድል ፈንታዬ፤* መዝሙረኛው ካህን ወይም ሌዋዊ መሆኑን ይጠቍማል (73፥26 እና ማብ ይመ)።

119፥58 *ልቤ፤* የ4፥7 ማብ ይመ።

119፥61 *ገመድ ተተበተበብኝ፤* ቢጨቍኑኝ፣ ቢያሠቃዩኝ ማለት ነው።

[62]ስለ ጻድቅ ሥርዐትህ፣
በእኩለ ሌሊት ላመሰግንህ እነሣለሁ።
[63]እኔ ለሚፈሩህ ሁሉ፣
ሥርዐትህንም ለሚጠብቁ ባልንጀራ ነኝ።
[64]እግዚአብሔር ሆይ፤ ምድር በምሕረትህ
ተሞላች፤
ሥርዐትህን አስተምረኝ።

ጠ ጤት

[65]እግዚአብሔር ሆይ፤ እንደ ቃልህ፣
ለአገልጋይህ በጎ ውለሃል።
[66]በትእዛዛትህ አምናለሁና፣
በጎ ማስተዋልንና ዕውቀትን አስተምረኝ።
[67]እንዲያው ሳይቸግረኝ መንገድ ስቼ
ሄድሁ፤
አሁን ግን ቃልህን እጠብቃለሁ።
[68]አንተ መልካም ነህ፤ የምታደርገው
መልካም ነው፤
እንግዲህ ሥርዐትህን አስተምረኝ።
[69]እብሪተኞች ስሜን በሐሰት አጠፉ፤
እኔ ግን ትእዛዝህን በፍጹም ልብ
እጠብቃለሁ።
[70]ልባቸው የሰባና የደነደነ ነው፤
እኔ ግን በሕግህ ደስ ይለኛል።
[71]ሥርዐትህን እማር ዘንድ፣
በመከራ ውስጥ ማለፌ መልካም ሆነልኝ።
[72]ከአእላፋት ብርና ወርቅ ይልቅ፣
ከአፍህ የሚወጣው ሕግ ይሻለኛል።

የ ዮድ

[73]እጆችህ ሠሩኝ፤ አበጃጁኝም፤
ትእዛዛትህን እንድማር ማስተዋልን
ስጠኝ።
[74]ቃልህን ተስፋ አድርጌአለሁና፣
የሚፈሩህ እኔን አይተው ደስ
ይበላቸው።
[75]እግዚአብሔር ሆይ፤ ፍርድህ የጽድቅ
ፍርድ፣
ያስጨነቅኸኝም በታማኝነት እንደ ሆነ
ዐወቅሁ።
[76]ለአገልጋይህ በገባኸው ቃል መሠረት፣
ምሕረትህ ለመጽናናት ትሁነኝ።
[77]ሕግህ ደስታዬ ነውና፣
በሕይወት እኖር ዘንድ ቸርነትህ
ትምጣልኝ።
[78]እብሪተኞች ያለ ምክንያት በደል
አድርሰውብኛልና ይፈሩ፤
እኔ ግን ትእዛዛትህን አሰላስላለሁ።
[79]አንተን የሚፈሩህ፣
ምስክርነትህንም የሚያውቁ ወደ
እኔ ይመለሱ።
[80]እኔ እንዳላፍር፤
ልቤ በሥርዐትህ ፍጹም ይሁን።

ከ ካፍ

[81]ነፍሴ ማዳንህን እጅግ ናፈቀች፤
ቃልህንም ተስፋ አደርጋለሁ።
[82]"መቼ ታጽናናኛለህ?" እያልሁ፣
ዐይኖቼ ቃልህን በመጠባበቅ ደከሙ።
[83]ጢስ የጠጣ የወይን አቍማዳ ብመስልም፣
ሥርዐትህን አልረሳሁም።
[84]የባሪያህ ዕድሜ ስንት ቢሆን ነው?
ታዲያ፣ በሚያሳድዱኝ ላይ
የምትፈርደው መቼ ይሆን?

119፥62 ቍ7:55፤ሐሥ16፥25
119፥63 ቍ56፤ መዝ15፥4፤101፥6-7፤103፥11፤111፥10
119፥64 ቍ12:108፤መዝ33፥5
119፥65 ቍ9:17፤ መዝ125፥4፤50፥2፤59፥11፤ሚክ2፥7
119፥66 መዝ51፥6
119፥67 ቍ17፤ መዝ95፥10፤116፥10፤ ኤር8፥4
119፥68 ዘፀ18፥20፤ መዝ100፥5፤106፥1፤107፥1፤135፥3
119፥69 ኢዮ13፥4፤ መዝ109፥2
119፥70 መዝ17፥10 ኢሳ29፥13፤ሐሥ28፥27
119፥71 ቍ67:75
119፥72 ኢዮ28፥17፤መዝ19፥10
119፥73 ዘፍ1፥27፤ ኢዮ4፥17፤10፥8፤መዝ138፥8፤139፥13-16
119፥74 ቍ9፤መዝ34፥2፤130፥5
119፥75 ቍ7:138:172፤ዕብ12፥5-11
119፥76 ቍ41፤ መዝ6፥4
119፥77 ቍ47፤ መዝ90፥13፤103፥13
119፥78 ቍ51:86:161፤መዝ35፥19፤ ኤር50፥32
119፥79 ቍ27:125
119፥80 ቍ1:6፤ ዘፍ26፥5፤1ነገ8፥61
119፥81 ቍ20:43:123፤መዝ84፥2
119፥82 ቍ41:123፤መዝ6፥7፤69፥3፤ሰቆ2፥11 119፥83 ቍ61
119፥84 ቍ51፤ መዝ6፥3፤ኤር12፥3፤15፥15፤20፥11፤ራእ6፥10

119፥62 *ላመሰግንህ፤* የመዝ100 ርእስ ማብ ይመ። *ጻድቅ፤* የቍ7 ማብ ይመ።

119፥63 *ባልንጀራቸው፤* የቍ53 ማብ ይመ።

119፥65 *በጎ ውለሃል፤* ከቍ68 ጋር ያነጻጽሩ። 31፥19፤ 86፥17 እና ማብ ይመ። *ቃልህ፤* የቍ25 ማብ ይመ።

119፥66 *አምናለሁና፤* ስለምመካ ማለት ነው፤ የእግዚአብሔር ትእዛዞች የሚያታልሉ፣ የሚሸነግሉ አይደሉም (የቍ29 ማብ ይመ)፤ ወይም የሚለዋወጡ አይደሉም (የቍ52 ማብ ይመ)።

119፥67 *ሳይቸግረኝ፤* በእግዚአብሔር እጅ ማለት ነው (ቍ71 ይመ፤ እንዲሁም የቍ25 ማብ ይመ)። *ለቃልህ፤* የቍ11 ማብ ይመ።

119፥69 *እብሪተኞች፤* የቍ21 ማብ ይመ።

119፥70 *የሰባና የደነደነ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም ድድር ያለ ማለት ነው። ከዚሁ ጋር ተመሳሳይ የሆነ አገላለጽ በኢሳ 6፥10፤ በኤር5፥28 ላይ ይገኛል (እንዲሁም 17፥10 ይመ)።

119፥72 *ከአእላፋት ብርና ወርቅ ይልቅ፤* ቍ14:57:111:162 ይመ።

*119፥73-80፤* እብሪተኞች ያፍሩና አንተን የሚፈሩ ከእኔ ጋር ሐሤት ያደርጉ ዘንድ ጽድቅ የሆኑትን ሕጎችህን እንድጠብቅ ፍጹም አድርገህ ሥራኝ (አበጃጀኝ)፤ የስንኞቹ ማእከላዊ አወቃቀር ተመሳሳይ ነው፤ ከቍ73 እና 80፤74 እና79፤ 75 እና78፤ 76 እና 77 ጋር ያነጻጽሩ።

119፥73 *ማስተዋልን፤* እኔን በሠራህ ጊዜ የጀመርኸውን ሥራ ከፍጻሜ ለማድረስ የሚያስፈልገኝ ይህ ማስተዋል ነው ማለቱ ነው።

119፥74 *የሚፈሩህ፤* ቍ79 ይመ። እንዲሁም የ34፥8-14 ማብ ይመ። *እኔን አይተው፤* ፍጹም ሆኜ በተሠራሁ ጊዜና አንተን ለሚፈሩት የምትሰጠውን በረከት አግኝቼ ደስ በተሰኘሁ ጊዜ ማለት ነው። *ቃልህን፤* የቍ25 ማብ ይመ።

119፥75 *ፍርድህ፤* ቃሉ በዕብራይስጥ ሚሽፓቲም ነው፤ ከዚህ በታች ያሉት ቍጥሮች እንደሚያመለክቱት እግዚአብሔር ከአገልጋዮቹ ጋር ካለው ግንኙነት አንጻር የሚሰጠውን ትክክለኛ ውሳኔ የሚያሳይ ነው (ቍ84 እና ማብ ይመ)። *ያስጨነቅኸኝም፤* ቍ67:71 ይመ።

119፥76 *ምሕረትህ፤* የ6፥4 ማብ ይመ። *ለመጽናናት፤* በተጨነቅሁ ጊዜ።

119፥77 *በሕይወት እኖር ዘንድ፤* በጭንቅ ውስጥ ሳለሁ እንዳልጠፋ ማለት ነው።

119፥78 *እብሪተኞች፤* የቍ21 ማብ ይመ። *ይፈሩ፤* እኔን ለኀፍረት እንደዳረጉኝ እነርሱም እንዲሁ ይድረስባቸው ማለቱ ነው (የ5፥10 ማብ ይመ)። *በደል አድርሰውብኛልና፤* የቍ25፥10 ማብ ይመ።

119፥79 *ወደ እኔ ይመለሱ፤* ቍ63 እና የቍ53 ማብ ይመ።

119፥80 *ልቤ፤* የ4፥7 ማብ ይመ። *እንዳላፍር፤* የቍ6 ማብ ይመ።

*119፥81-88፤* በሰጠኸኝ ተስፋ መሠረት ከጭንቀቴና ከአሳዳጆቼ አድነኝ፤ እኔም ለሥርዐቶችህ እታዘዛለሁ። የመዝሙሩ የመጀመሪያው አጋማሽ የሆነው ይህ የመጨረሻው አንጓ እንደ መዝሙሩ መደምደሚያ አንጓ ሁሉ የእግዚአብሔርን ርዳታ በሚጠይቅ ጸሎት የተሞላ ነው (የቍ25 ማብ ይመ)።

119፥81 *ነፍሴ፤* የ6፥3 ማብ ይመ።

119፥82 *ዐይኖቼ ደከሙ፤* የ6፥7 ማብ ይመ።

119፥83 *ጢስ የጠጣ የወይን አቍማዳ፤* እሳት ከሚነድበት ምድጃ በላይ ተሰቅሎ ጢስ የጠገበ አቍማዳ ጥቀርሻ እንደሚያደራበት ሁሉ መዝሙረኛውም ይህንኑ የመሰለ አስከፊ ነገር ደርሶበታል።

119፥84 *ዕድሜ ስንት ቢሆን ነው?* ቃል በቃል ሲተረጐም "የባርያህ ዘመኑ ስንት ነው?" የሕይወት ዘመኔ አጭር ስለ ሆነች የአሳዳጆቼን ቅጣት አታዘግይ። *የምትፈርደው፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "የፍትህ ውጤት" ማለት ነው ("ፍትህ" ለሚለው ቃል የዕብራይስጡ "ሚሽፋት" ነው፤ በቍ7 ላይ "ሕጎች" ተብሎአል። እንዲሁም የ5፥10 ማብ ይመ)።

85በሕግህ መሠረት የማይሄዱ፣
እብሪተኞች ጕድጓድ ቈፈሩልኝ::
86ትእዛዛትህ ሁሉ አስተማማኝ ናቸው፤
ሰዎች ያለ ምክንያት አሳደውኛልና
ርዳኝ::
87ከምድር ላይ ሊያስወግዱኝ ጥቂት
ቀራቸው፤
እኔ ግን ትእዛዛትህን አልተውሁም::
88እንደ ምሕረትህ መልሰህ ሕያው
አድርገኝ፤
እኔም የአፍህን ምስክርነት እጠብቃለሁ::

ን ላሜድ

89እግዚአብሔር ሆይ፤ ቃልህ በሰማይ፣
ለዘላለም ጸንቶ ይኖራል::
90ታማኝነትህ ከትውልድ እስከ ትውልድ
ሁሉ ይኖራል፤
ምድርን መሠረትሃት፤ እርሷም ጸንታ
ትኖራለች::
91ሁሉም አገልጋይህ ነውና፣
በሕግህ መሠረት እስከ ዛሬ ድረስ
ጸንተው ይኖራሉ::
92ሕግህ ደስታዬ ባይሆን ኖሮ፣
በመከራዬ ወቅት በጠፋሁ ነበር::
93በእርሱ ሕያው አድርገኸኛልና፣
ትእዛዝህን ከቶ አልረሳም::
94እኔ የአንተ ነኝ፤ እባክህ አድነኝ፤
ሕግህንም ፈልጌአለሁና::
95ክፉዎች ሊያጠፉኝ አድብተዋል፤
እኔ ግን ምስክርነትህን አሰላስላለሁ::
96ለፍጹምነት ሁሉ ዳርቻ እንዳለው አየሁ፤
ትእዛዝህ ግን እጅግ ሰፊ ነው::

ם ሜም

97አቤቱ፤ ሕግህን ምንኛ ወደድሁ!
ቀኑን ሙሉ አሰላስለዋለሁ::
98ትእዛዛትህ ምን ጊዜም ስለማይለዩኝ፣
ከጠላቶቼ ይልቅ አስተዋይ አደረጉኝ::
99ምስክርነትህን አሰላስላለሁና፣
ከአስተማሪዎቼ ሁሉ የላቀ አስተዋይ
ልብ አገኘሁ::
100መመሪያህን ተከትዬ እሄዳለሁና፣
ከሽማግሌዎች ይልቅ አስተዋይ ሆንሁ::
101ቃልህን እጠብቅ ዘንድ፣
እግሬን ከክፉ መንገድ ሁሉ ከለከልሁ::
102አንተው ራስህ አስተምረኸኛልና፣
ከድንጋጌህ ዘወር አላልሁም::
103ቃልህ ለምላሴ ምንኛ ጣፋጭ ነው!
ለአፌም ከማር ወለላ ይልቅ ጣዕም
አለው::
104ከመመሪያህ ማስተዋልን አገኘሁ፤
ስለዚህ የሐሰትን መንገድ ሁሉ ጠላሁ::

נ ኖን

105ሕግህ ለእግሬ መብራት፣
ለመንገዴም ብርሃን ነው::
106የጽድቅ ሕግህን ለመጠበቅ፤
ምያለሁ፤ ይህንኑ አጸናለሁ::
107እጅግ ተቸግሬአለሁ፤
እግዚአብሔር ሆይ፤ እንደ ቃልህ
መልሰህ ሕያው አድርገኝ::
108እግዚአብሔር ሆይ፤ ፈቅጄ ያቀረብሁትን
የአፌን የምስጋና መሥዋዕት
ተቀበል፤
ሕግህንም አስተምረኝ::

119፥85 ቍ51፤ መዝ35፥7፤57፥6፤ኤር 18፥20፡22
119፥86 ቍ78፡138 ፤መዝ7፥1፤109፥26
119፥87 ቍ150፤ ኢሳ1፥4፡28፤58፥2፤ 59፥13
119፥88 ቍ2፡100፡ 124፡129፡134፡168፤ መዝ41፥2፤51፥1፤ 109፥26
119፥89 ቍ111፡ 144፤መዝ111፥8፤ኢሳ 51፥6፤ማቴ5፥18፤ 1ጴጥ1፥25
119፥90 ኢዮ8፥19፤ መዝ36፥5፤45፥17፤ 148፥6
119፥91 መዝ104፥ 2-4፤ኤር31፥35፤ 33፥25
119፥92 ቍ50፡67፤ መዝ37፥4፤112፥1
119፥93 ቍ83፤ መዝ103፥5
119፥94 ቍ45፡ 146፤መዝ54፥1፤116፥ 4፤ኤር17፥14፤31፥18 ፤42፥11
119፥95 ቍ99፤ መዝ69፥4
119፥96 መዝ19፥7
119፥97 ቍ15፡47
119፥98 ቍ130፤ ዘዳ4፥6፤መዝ19፥7፤ 2ጢሞ3፥15
119፥99 ቍ15
119፥100 ቍ56፤ ዘዳ6፥17
119፥101 ቍ57፤ ምሳ1፥15
119፥102 ዘዳ4፥5፤ 17፥20
119፥103 መዝ19፥ 10፤ምሳ24፥13-14
119፥104 ቍ128፤ መዝ111፥10
119፥105 ቍ130፤ ምሳ6፥23፤20፥27፤2ጴጥ1፥19
119፥106 ቍ7፤ ነህ10፥29
119፥107 ቍ25
119፥108 ቍ64፤ መዝ51፥15፤63፥5፤71፥8፤109፥30

119፥85 *እብሪተኞች፤* የቍ21 ማብ ይመ:: *የማጥመጃ ጕድጓድ ቈፈሩልኝ፤* ምናልባት የደረሰበትን ሐሜት ሳያሳይ አይቀርም፤ መዝሙረኛው ክፉ ኀጢአት ባይሠራ ኖሮ እንዲህ ባለው መከራ ውስጥ አይገባም ነበር በማለት ስሙን በአደባባይ ያጠፉት መሆኑን ሊያመለክት ይችላል:: *በሕግህ መሠረት፤* ዘፀ 20፥16 ይመ::

119፥86 *አስተማማኝ፤* በቍ29 ማብ ላይ "በማታለል መንገድ" የሚለውን ይመ::

119፥88 *ምሕረትህ፤* የ6፥4 ማብ ይመ::

*119፥89-91፤* የእግዚአብሔር ሉዓላዊነት የማይሻረው ቃል ዓለምን ይገዛል፤ በሥርዐትም ይመራዋልም:: (እነዚህ የመዝሙሩ ሁለተኛ ክፍል የመጀመሪያው ሦስት ቍጥሮች የሚያስተምሩት ስለ ጠቅላላ እውነት ነው፤ ከቍ1-3 ጋር ያነጻጽሩ)::

119፥89 *ቃልህ፤* በዚህ ቦታ የሚያመለክተው ሁሉን ነገር የፈጠረበትን፣ በሥርዐት የሚመራብትንና የሚያስተዳድርበትን ቃል ነው (33፥4፡6፤ 107፥20፤ 147፥15፡18 ይመ):: በሰማያት ጸንቶ ይኖራል፤ ጸንቶ የሚኖረው የሰማያትና የምድር ሥርዐት (ቍ90)፣ የእግዚአብሔርን ቃል (ማለትም "ሕግጋቱ" ቍ91)፣ እርግጠኛነት ያውጃል (19፥1-4)፤ ይህም ሥነ-ፍጥረቱን ሁሉ ደግፎ የያዘበትና የሚገዛበት ሥልጣኑ ሲሆን ጸንቶ የሚኖርና (ዘላለማዊና) ታማኝ ቃል ነው ("ታማኝነትህ" ቍ90):: እንግዲህ የእግዚአብሔር ሰው ልዩ መገለጥና ታማኝ በሆነው በእግዚአ ብሔር ቃል ላይ ያለውን ጽኑ እምነት (ሕጎቹንና ተስፋዎቹን) የሚያረጋግጥለት ታላቁ እውነታ ይህ ነው (የ93፥5፤ የ96፥10 ማብ ይመ:: እንዲሁም በቍ29 ማብ ላይ "በማታለል መንገድ" የሚለውን ሐረግ ይመ)::

119፥90 *ታማኝነትህ፤* ቡተዘዋዋሪ የእግዚአብሔር ቃል የሚያመለክት ነው (ቍ89 እና ማብ ይመ)::

119፥92 *በመከራዬ ወቅት በጠፋሁ ነበር፤* ከሕግህ (ቍ67፡71፤ እንዲሁም የ65-72 ማብ ይመ)፣ የሕይወትን መንገድ መማር ባልቻልሁ ነበር (ቍ93 ይመ)::

119፥95 *ክፉዎች፤* የቍ21 ማብ ይመ ("እብሪተኞች") እኔን ለማጥፋት አድብተዋል፤ የቍ25 ማብ ይመ ("ወድቀዋል")::

119፥96 *ለፍጹምነት፤* ምናልባት በሙሉነት ደረጃ ፍጹም ነትን የሚያመለክት አነጋገር ነው:: *ትእዛዝህ ... ሰፊ ነው፤* ቃል በቃል ሲተረጐም ወሰን የሌላቸው ማለት ነው:: እነዚህም ተዝቀው የማያልቁ፣ ለሕይወት ጠቃሚ የሆነ የዕውቀት ምክር የሚገኝባቸው ናቸው (ቍ97-100 ይመ)::

*119፥97-104፤* የእግዚአብሔርን ሕግ ማሰላሰል ከፍተኛ ጥበብን ያስገኛል::

119፥98 *ከጠላቶቼ፤* እነዚያ እብሪተኞች ማለት ነው (የቍ21 ማብ ይመ)፤ እነርሱም በዚህ ዓለም ጥበብ የሚታመኑ፣ የሚመኩ ናቸው::

119፥99 *ከአስተማሪዎቼ፤* ሰዎችን ያመለክታል::

119፥100 *ከሽማግሌዎች፤* በልምድ ብዙ ዕውቀት ያካበቱ አረጋውያን (የዘፀ3፥16 ማብ ይመ)::

119፥102 *አንተው ራስህ አስተምረኸኛልና፤* በሕጎችህ አማካይነት::

119፥103 *ቃልህ፤* እዚህ ላይ ሕጎችህ ቢባል የተገባ ሳይሆን አይቀርም (ቍ67፡133፡158፡172 እና የቍ11 ማብ ይመ)::

119፥104 *የሐሰትን መንገድ ሁሉ ጠላሁ፤* የቍ53 ማብ ይመ::

119፥105 *መብራት ...ብርሃን፤* ያለ እነዚህ መኖር፣ በጨለማ ውስጥ በዳበሳ ብቻ መንከላወስ ማለት ነው::

119፥106 *ምያለሁ ይህንኑ አጸናለሁ፤* ቃል ኪዳን መግባት ማለት ነው (ነህ10፥29 ይመ)::

*119፥107፤* ቍ25 እና ማብ ይመ::

[109]ነፍሴ ዘወትር አደጋ ላይ ናት፤
ሕግህን ግን አልረሳሁም።
[110]ክፉዎች ወጥመድ ዘረጉብኝ፤
እኔ ግን መመሪያህን አልተሳለፍሁም።
[111]ምስክርነትህ የዘላለም ውርሴ ናት፤
ልቤ በዚህ ሐሤት ያደርጋልና።
[112]ትእዛዝህን ለዘላለም፣ እስከ ወዲያኛው
ለመፈጸም፣
ልቤን ወደዚያው አዘንበልሁ።

ዐ ሳምኬት

[113]መንታ ልብ ያላቸውን ጠላሁ፤
ሕግህን ግን ወደድሁ።
[114]አንተ መጠጊያዬና ጋሻዬ ነህ፤
ቃልህን በተስፋ እጠብቃለሁ።
[115]የአምላኬን ትእዛዛት እጠብቅ ዘንድ፣
እናንት ክፉ አድራጊዎች፣ ከእኔ ራቁ።
[116]እንደ ቃልህ ደግፈኝ፤ እኔም ሕያው
እሆናለሁ፤
ተስፋዬም መና ቀርቶ አልፈር።
[117]ያለ ሥጋት እቀመጥ ዘንድ ደግፈህ
ያዘኝ፤
ሥርዐትህንም ዘወትር እመለከታለሁ።
[118]መሰሪነታቸው በከንቱ ነውና፣
ከሥርዐትህ ውጭ የሚሄዱትን ሁሉ
ወዲያ አስወገድሃቸው።
[119]የምድርን ክፉዎች ሁሉ እንደ ጥራጊ
አስወገድሃቸው፤
ስለዚህ ምስክርህን ወደድሁ።
[120]ሥጋዬ አንተን በመፍራት
ይንቀጠቀጣል፤
ፍርድህንም እፈራለሁ።

ፀ ፄ

[121]ፍትሕና ጽድቅ ያለበትን ሠርቻለሁ፤
ለሚጨቍኑኝ አሳልፈህ አትስጠኝ።

119፥109 ቍ61፤ መሳ12፥3
119፥110 ቍ10፤ መዝ25፥15፤64፥5፤ ኢሳ8፥14፤አሞ3፥5
119፥111 ቍ14፡162
119፥112 ቍ33፤ መዝ108፥1
119፥113 ቍ47፤ 1ነገ18፥21፤ያዕ1፥8፤ 4፥8
119፥114 ቍ43፤ ዘፍ15፥1፤መዝ18፥2
119፥115 መዝ6፥8
119፥116 ቍ41፤ መዝ18፥35፤41፥3፤ 55፥22፤ኢሳ46፥4፤ ሮሜ5፥5
119፥117 ቍ6፤ መዝ34፥4፤ኢሳ 41፥10፤46፥4
119፥118 ቍ10
119፥119 ቍ47፤ ኢሳ1፥22፡25፤ሕዝ 2፥18፡19
119፥120 ኢሱ 24፥14፤ኢዮ4፥14፤ ኢሳ64፥2፤ኤር10፥7 ፤ዕን3፥2
119፥121 2ሳሙ 8፥15፤ኢዮ27፥6
119፥122 ቍ21፡ 121፡134፤ኢዮ17፥3፤ መዝ106፥42
119፥123 ቍ81፡82 ፤ኢሳ38፥14
119፥124 ቍ12፡88 ፤መዝ25፥7
119፥125 ቍ79፤ መዝ116፥16
119፥126 ዘኍ15፥31
119፥127 ቍ47፤ ኢዮ3፥21፤መዝ19፥10
119፥128 ቍ104፡ 163፤መዝ19፥8፤31፥6 ፤ምሳ13፥5

[122]ለባሪያህ በጎነት ዋስትና ሁን፤
እብሪተኛ እንዲጨቍኑኝ አትፍቀድላቸው።
[123]ዐይኖቼ ማዳንህን፣
የጽድቅ ቃልህን በመጠባበቅ ደከሙ።
[124]ለባሪያህ እንደ ምሕረትህ መጠን
አድርግ፤
ሥርዐትህንም አስተምረኝ።
[125]እኔ ባሪያህ ነኝ፤
ምስክርነትህን ዐውቅ ዘንድ ማስተዋልን
ስጠኝ።
[126]እግዚአብሔር ሆይ፤
ሕግህ እየተጣሰ ነውና፣
ጊዜው አንተ የምትሠራበት ነው።
[127]ስለዚህ ከወርቅ፣ ከንጹሕ ወርቅ ይልቅ፣
ትእዛዛትህን ወደድሁ።
[128]መመሪያህ ሙሉ በሙሉ ልክ ነው
አልሁ፤
ስለዚህ የሐሰትን መንገድ ሁሉ ጠላሁ።

ፀ ፌ

[129]ምስክርነትህ ሁሉ ድንቅ ነው፤
ስለዚህ ነፍሴ ትጠብቀዋለች።
[130]የቃልህ ትርጓሜ ያበራል፤
አላዋቂዎችንም አስተዋዮች ያደርጋል።
[131]ትእዛዝህን ናፍቄአለሁና፣
አፌን ከፈትሁ አለከለክሁም።
[132]ስምህን ለሚወዱ ማድረግ ልማድህ እንደ
ሆነ ሁሉ፣
ወደ እኔ ተመልሰህ፣ ምሕረት
አድርግልኝ።
[133]አካሄዴን እንደ ቃልህ ቀና አድርግልኝ፤
ኀጢአትም በላዬ እንዲሠለጥን
አትፍቀድ።

119፥129 ቍ18፡ 22፡88 119፥130 ቍ105፤ መዝ19፥7 119፥131 ቍ20፤መዝ42፥1 119፥132 2ሳሙ24፥14፤መዝ 5፥11 ፤6፥4፤9፥13፤2ሳሙ24፥14 119፥133 ቍ9፡11፤ሮሜ6፥16

119፥109 *ነፍሴ ... አደጋ ላይ ናት፤* ማስፈራራትና ጥላቻ ቢኖርበትም እንኳ (በተለይ ቍ23፡46፡161 ይመ)፣ የእግዚአብሔርን ሕግ በይፋ ያከብራል።

119፥110 *ወጥመድ ዘረጉብኝ፤* ቍ85 እና ማብ ይመ።

119፥111-112 *ልቤን ... ልቤ፤* የ4፥7 ማብ ይመ።

119፥111 *ውርሴ፤* ሕይወቴ የሚያስፈልጋትን ነገር የምታገኘው ርስቷ ከሆነው ከእግዚአብሔር ከተሰጣት ሀብትና ንብረት ነው (ቍ57-64 ይመ)።

119፥113 *መንታ ልብ ያላቸውን ጠላሁ፤* ቍ115 ይመ፤ እንዲሁም የቍ53 ማብ ይመ። ሐሳቡ የተከፈለ ሰው በሚያደርገው ነገር ሁሉ ወላዋይ ነው፤ ቍርጦ አንድ ነገር መወሰን አይችልም (ያዕ1፥8)።

119፥114 *ቃልህን፤* የቍ25 ማብ ይመ።

119፥118 *አስወገድሃቸው፤* ወይም "ታርገፈግፋቸዋለህ" (ትነቀንቃቸዋለህ) ወይም "ታቃልላቸዋለህ" ማለት ነው። *መሠሪነታ ቸው፤* ምናልባት የማታለል (የቍ29 ማብ ይመ) መንገዳቸውን ወይም የሚያታልሉበትን መንገድ ሳያመለክት አይቀርም።

119፥119 *ጥራጊ፤* ከቀለጠ ብረት የሚወጣ ቈሻሻ ነገር ነው። በዕብራይስጡ ይህ ቃል በቍ118 ላይ "ስተው የሚወጡትን" የሚለው ቃል ከሚሰጠው ትርጕም ጋር ተመሳሳይ ነው። በአማርኛ ቅኔ አንዱ ቃል ሰምና ወርቅ ሆኖ ሁለት ዐይነት ትርጕም እንደሚሰጥ ማለት ነው። የሳቱ ሰዎች እንደ ጥራጊ ይቈጠራሉ፤ እንደ ቈሻሻና ጕድፍ ይወገዳሉ።

119፥120 *ሥጋዬ ... ይንቀጠቀጣል፤* ለእግዚአብሔር ካለው ጥልቅ አክብሮት የተነሣ ይንቀጠቀጣል።

*119፥121-128፤* ታማኝ ባሪያህ እንደ መሆኔ ከሚያሳድዱኝና ከሚጨቍኑኝ ሰዎች እንድትታደገኝ ወደ አንተ እጸልያለሁ፤ የእግዚአብሔርን ማዳን ወይም ትድግና በጽኑ የሚሻ ሌላ ጸሎት ነው (ቍ81-88 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም የቍ25 ማብ ይመ)።

119፥121 *ፍትሕና ጽድቅ ያለበትን፤* የእግዚአብሔርን ሕግ ማለት ነው።

*119፥122፤* በዚህ መዝሙር ውስጥ ከእግዚአብሔር ቃል ጋር በቀጥታ ወይም በተዘዋዋሪ ጨርሶ የማይገናኝ ቍጥር ነው (በቍ 90፡121፡132 ላይ እንዳለው ዐይነት ማለት ነው፤ እንዲሁም የቍ75 ማብ ይመ)። *እብሪተኞች፤* የቍ21 ማብ ይመ።

119፥123 *ዐይኖቼ ... ደከሙ፤* የ6፥7 ማብ ይመ።

119፥124 *ምሕረትህ፤* የ6፥4 ማብ ይመ።

119፥126 *የምትሠራበት፤* ባሪያውን ለመታደግ ወይም በሕግ አፍራሾች ላይ ለመፍረድ ወይም ደግሞ ሁለቱንም ለማድረግ ሊሆን ይችላል።

119፥127 *ከወርቅ ... ይልቅ፤* ቍ14፡57፡72፡111 ይመ።

119፥129 *ድንቅ፤* ቍ18 እና ማብ ይመ።

119፥130 *ትርጓሜ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "መክፈት" ማለት ሲሆን በዚህ ቦታ የያዘው ፍቺ (1) የቃልህ መገለጥ (2) የቃልህ ትርጓሜ (በ49፥4 ላይ "እገልጣለሁ" የሚለውን ይመ) (3) የቃልህን ወደ ልቤ ጠልቆ መግባት የሚሉ ናቸው። *ገሮችንም፤* 19፥7 እና ማብ ይመ።

119፥132 *ማድረግ ልማድህ እንደ ሆነ ሁሉ፤* ቃሉ በዕብራይስጥ "ሚሽፓት" ማለት ነው፤ "አደራረግህ" (ወይም "አሠራርህ") ማለት ሲሆን በተዘዋዋሪ የእግዚአብሔርን ሕግ ያመለክታል (የቍ122 ማብ ይመ፤ እንዲሁም የቍ7 ማብ ይመ)።

119፥134፡154 *ታደገኝ፤* ተቤዠኝ ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ ነው።

[134]ትእዛዝህን መጠበቅ እንድችል፣
ከሰዎች ጥቃት ታደገኝ።
[135]በባሪያህ ላይ ፊትህን አብራ፤
ሥርዐትህንም አስተምረኝ።
[136]ሕግህ ባለመከበሩ፤
እንባዬ እንደ ውሃ ይፈሳል።

ጻ ጻዴ

[137]እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ ጻድቅ ነህ፤
ፍርድህም ትክክል ነው።
[138]ምስክርነትህን በጽድቅ አዘዝህ፤
እጅግ አስተማማኝም ነው።
[139]ጠላቶቼ ቃልህን ዘንግተዋልና፣
ቅናት አሳረረኝ።
[140]ቃልህ እጅግ የነጠረ ነው፤
ባሪያህም ወደደው።
[141]እኔ ታናሽና የተናቅሁ ነኝ፤
ነገር ግን መመሪያህን አልዘነጋሁም።
[142]ጽድቅህ ዘላለማዊ ጽድቅ ነው፤
ሕግህም እውነት ነው።
[143]መከራና ሥቃይ ደርሶብኛል፤
ነገር ግን ትእዛዝህ ደስታዬ ነው።
[144]ምስክርነትህ ለዘላለም የጽድቅ ምስክርነት ነው፤
በሕይወት እኖር ዘንድ ማስተዋልን ስጠኝ።

ፆ ቆፍ

[145]እግዚአብሔር ሆይ፤ በፍጹም ልቤ
እጮኻለሁና መልስልኝ፤
ሥርዐትህንም እጠብቃለሁ።
[146]ወደ አንተ እጣራለሁና አድነኝ፤
ምስክርነትህንም እጠብቃለሁ።
[147]ትረዳኝ ዘንድ ጎሕ ሳይቀድ ተንሥቼ
እጮኻለሁ፤
ቃልህንም ተስፋ አደርጋለሁ።
[148]ቃልህን አሰላስል ዘንድ፣
ዐይኔ ሌሊቱን ሙሉ ሳይከደን ያድራል።
[149]እንደ ቸርነትህ መጠን ድምፄን ስማ፤
እግዚአብሔር ሆይ፤ እንደ ሕግህ
መልስህ ሕያው አድርገኝ።
[150]ደባ የሚያውጠነጥኑ ወደ እኔ
ቀርበዋል፤
ከሕግህ ግን የራቁ ናቸው።
[151]እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ ግን ቅርብ
ነህ፤
ትእዛዛትህም ሁሉ እውነት ናቸው።
[152]ለዘላለም እንደ መሠረትሃቸው፣
ከጥንት ምስክርነትህ ተረድቻለሁ።

ገ ሬስ

[153]ሕግህን አልረሳሁምና፣
ሥቃዬን ተመልከት፤ ታደገኝም።
[154]ተሟገትልኝ፤ አድነኝም፤
እንደ ቃልህም ሕያው አድርገኝ።
[155]ሥርዐትህን ስለማይሹ፣
ድነት ከክፉዎች የራቀ ነው።
[156]እግዚአብሔር ሆይ፤ ርኅራኄህ ታላቅ
ነው፤
እንደ ሕግህ ሕያው አድርገኝ።
[157]የሚያሳድዱኝ ጠላቶቼ ብዙዎች ናቸው፤
እኔ ግን ከምስክርህ ዘወር አላልሁም።
[158]ቃልህን አይጠብቁምና፣
ከዳተኞችን አይቼ አርቃቸዋለሁ።
[159]መመሪያህን እንዴት እንደምወድ
ተመልከት፤
እግዚአብሔር ሆይ፤ እንደ ምሕረትህ
ሕያው አድርገኝ።
[160]ቃልህ በሙሉ እውነት ነው፤
ጻድቅ የሆነው ሕግህም ዘላለማዊ ነው።

ሠ ሳን

[161]ገዦች ያለ ምክንያት አሳደዱኝ፤
ልቤ ግን ከቃልህ የተነሣ እጅግ ፈራ።
[162]ትልቅ ምርኮ እንዳገኘ ሰው፤

119፥134 ቍ56፡88፡122
119፥135 ቍ12፤ ዘኍ6፥25፤ መዝ4፥6፤ 67፥1፤80፥3
119፥136 ቍ158፤ መዝ6፥6፤106፥25፤ ኢሳ22፥4፤42፥24፤ ኤር9፥1፡18፤13፥17፤ 14፥17፤ሰቆ1፥16፤ 34፥8፤ሕዝ9፥4
119፥137 ዘፀ9፥27 ፤ዕዝ9፥15፤ነህ9፥13
119፥138 ቍ75፡86 ፤መዝ19፥7
119፥139 መዝ69፥9 ፤ዮሐ2፥17
119፥140 ቍ47፤ ኢሱ23፥14፤ መዝ12፥6
119፥141 ቍ61፡ 134፤መዝ22፥6
119፥142 ቍ151፡ 160፤መዝ19፥7
119፥143 ቍ24፡ 47
119፥144 ቍ34
119፥145 ቍ10፡ 22፡55
119፥146 ቍ94
119፥147 መዝ5፥3 ፤57፥8፤108፥2
119፥148 መዝ63፥6
119፥149 ቍ40፡ 124፤መዝ27፥7
119፥150 መዝ37፥7
119፥151 ቍ142፤ መዝ34፥18፤ፊል4፥5
119፥152 ቍ7፡73 ፡89፤መዝ111፥8፤ሉቃ 21፥33
119፥153 መዝ3፥7 ፤13፥3፤44፥17
119፥154 ቍ25፡ 41፤1ሳሙ24፥15፤ መዝ35፥1፤ኤር50፥34 ፤ሚክ7፥9
119፥155 ቍ94፡ 118
119፥156 ቍ25፡ 149፤ነህ9፥27፤ ያዕ5፥11
119፥157 መዝ7፥1፤44፥18 119፥158 ቍ104፡136፤ዘፀ32፥19
119፥159 ቍ25፤መዝ41፥2 119፥160 ቍ89፤መዝ111፥8
119፥161 ቍ23፡120፡122፡157፤1ሳሙ24፥14-15
119፥162 ቍ111፤1ሳሙ30፥16፤ኢሳ 9፥3፤53፥12

119፥134 *ጥቃት፤* የቍ ጥር 25 ማብ ይመ ("ወድቄአለሁ")።
119፥135 *ፊትህን አብራ፤* የ13፥1 ማብ ይመ ("ፊትህን ሰውር")።
*119፥136፤* ቍ53 እና ማብ ይመ።
*119፥137-144፤* እግዚአብሔርና ሕጉ ጻድቅ ናቸው።
119፥137 *ጻድቅ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።
119፥138 *አስተማማኝም፤* ቍ142 ይመ። በቍ29 ማብ ይመ ("ከሽንገላ መንገድ")።
119፥139 *ቅናት፤* የቍ53 ማብ ይመ።
119፥140 *ቃልህ፤* ዕብራይስጡ ኢምራህ ይለዋል፤ ምናልባትም እዚህ ላይ ቃል ተብሎ ቢተረጐም የተሻለ ሳይሆን አይቀርም (የቍ11 ማብ ይመ)። *የነጠረ ነው፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "የተፈተነ" ማለት ሲሆን፣ የእግዚአብሔር ቃል ጥቅም የሌለውና አንድም ነገር አለመያዙን ወይም እጅግ ከፍ ያለ ዋጋና ጥቅም ያለው መሆኑን ያመለክታል።
119፥141 *ታናሽና የተናቅሁ፤* ከቍ143 ጋር ያነጻጽሩ። እንዲሁም የቍ25 ማብ ይመ።
119፥145-152 *ጌታ ሆይ፤ አድነኝ፤ እኔም ሕግህን እጠብቃለሁ፤* መዝሙሩ ሊፈጸም ሲቃረብ የእግዚአብሔርን ማዳን ወይም ትድግና ለማግኘት የሚደረገው ጸሎት ይበልጥ እየበረታና እያየለ ሲሄድ ይታያል (በቍ25 ማብ ላይ "ወድቄአለሁ" የሚለውን ይመ)።
119፥148 *ሌሊቱን ሙሉ፤* የመሳ7፥19 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ሰቆ2፥19 ይመ።
119፥149 *ቸርነትህ፤* የ6፥4 ማብ ይመ። *ሕግህ፤* ወይም "ፍርድህ" ማለት ነው (ይህም "ፍቅርህ" ለሚለው ቃል እንደ ማሟያ የሚያገለግል ነው)፤ በዕብራይስጡ ሚሽፓት ይባላል (የቍ75 ማብ ይመ)።
119፥150 *ከሕግህ ... የራቁ፤* ቍ21፡53፡85፡118፡126፡139፡155፡158 ይመ።
119፥151 *እውነት ናቸው፤* የቍ29 ማብ ይመ ("ከማታለል መንገድ")።
119፥152 *ለዘላለም ... ከጥንት፤* የቍ52 ማብ ይመ።
*119፥153-160፤* የቍ145-152 ማብ ይመ።
119፥155 *ከክፉዎች፤* የቍ21 ማብ ይመ ("እብሪተኞች")።
119፥156 *እንደ ሕግህ፤* ቍ149 እና ማብ ይመ።
119፥158 *ቃልህን፤* ዕብራይስጡ ኢምራ ይለዋል (የቍ11 ማብ ይመ)።
119፥160 *በሙሉ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ድምሩ" ማለት ነው (በመዝ137፥17 እንደ ተጻፈው ማለት ነው)። *እውነት፤* የቍ29 ማብ ይመ ("ከማታለል መንገድ")። *ዘላለማዊ፤* የቍ52 ማብ ይመ።
*119፥161-168፤* የቍ145-152 ማብ ይመ።
119፥161 *ገዦች፤* የቍ23 ማብ ይመ። *ልቤ፤* የ4፥7 ማብ ይመ።
119፥162 *ትልቅ ምርኮ፤* ቍ14፡72፡111 ይመ።

በቃልህ ደስ አለኝ።
[163]ሐሰትን እጠላለሁ፤ እጸየፋለሁ፤
ሕግህን ግን ወደድሁ።
[164]ጻድቅ ስለ ሆነው ሕግህ፤
በቀን ሰባት ጊዜ አመሰግንሃለሁ።
[165]ሕግህን የሚወዱ ብዙ ሰላም አላቸው፤
ዕንቅፋትም የለባቸውም።
[166]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ማዳንህን ተስፋ
አደርጋለሁ፤
ትእዛዝህንም እፈጽማለሁ።
[167]ነፍሴ ምስክርነትህን ትጠብቃለች፤
እጅግ እወደዋለሁና።
[168]መንገዴ ሁሉ በፊትህ ግልጽ ነውና፣
ሕግህንና ምስክርነትህን እጠብቃለሁ።

*ꡤ ታው*

[169]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ጩኸቴ ከፊትህ
ይድረስ፤
እንደ ቃልህም ማስተዋልን ስጠኝ።
[170]ልመናዬ ከፊትህ ይድረስ፤
እንደ ቃልህም ታደገኝ።
[171]ሥርዐትህን አስተምረኸኛልና፣
ከንፈሮቼ ምስጋናን አፈለቁ።
[172]ትእዛዛትህ ሁሉ የጽድቅ ትእዛዛት
ናቸውና፣
አንደበቴ ስለ ቃልህ ይዘምር።
[173]ትእዛዝህን መርጫለሁና፣
እጅህ እኔን ለመርዳት ዝግጁ ይሁን።
[174]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ማዳንህን ናፈቅሁ፤
ሕግህም ደስታዬ ነው።
[175]አመሰግንህ ዘንድ በሕይወት ልኑር፤
ሕግህም ይርዳኝ።
[176]እንደ ጠፋ በግ ተቅበዘበዝሁ፤
ትእዛዛትህን አልረሳሁምና፣
ባሪያህን ፈልገው።

## መዝሙር 120

### የሰላም ፀሮች

*መዝሙረ መዓርግ*

[1]በተጨነቅሁ ጊዜ ወደ *እግዚአብሔር*
ተጣራሁ፤
እርሱም መለሰልኝ።
[2]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከሐሰተኛ ከንፈር፣
ከአታላይ ምላስም አድነኝ።
[3]ሐሰተኛ አንደበት ሆይ፤ ምን ይከፈልህ?
ከዚህስ የባሰ ምን ይደረግብህ?
[4]በተሳለ የጦረኛ ቀስት፣
በግራር ከሰል ፍም ይቀጣሃል።
[5]በሜሼክ እኖራለሁና፣
በቄዳር ድንኳኖች መካከል እቀመጣለሁና
ወዮልኝ!
[6]ሰላምን በሚጠሉ መካከል፣
ነፍሴ እጅግ ብዙ ጊዜ ኖረች።
[7]እኔ ሰላም ፈላጊ ነኝ፤
እነርሱ ግን በተናገርሁ ጊዜ ጠብ ይሻሉ።

119፥163 ቍ47፡128
119፥164 ቍ7፡160
119፥165 ቍ11፤ መዝ37፥11፡24፤ ኢሳ26፥3፡12፤27፥5፤32፥17፤57፥19፤66፥12፤1ዮሐ2፥10
119፥166 ቍ81
119፥167 ቍ47
119፥168 ቍ2፡22፡56፡88፤ኢዮ10፥4፤23፥10፤መዝ139፥3፤ምሳ5፥21
119፥169 ቍ9፡34፤ኢዮ16፥18
119፥170 ቍ41፤1ነገ8፥30፤2ዜና6፥24፤መዝ3፥7፤22፥20፤28፥2፤59፥1፤140፥6፤143፥1
119፥171 መዝ51፥15፤63፥3፤94፥12፤ኢሳ2፥3፤ሚክ4፥2
119፥172 ቍ7፡75፤መዝ51፥14
119፥173 ኢሱ24፥22፤መዝ37፥24፤73፥23፤ኢሳ41፥10
119፥174 ቍ16፡24፡166
119፥175 ቍ116፡159፤ኢሳ55፥3
119፥176 ቍ10፤መዝ44፥17፤95፥10፤ኤር50፥17፤ሕዝ34፥11፤ሉቃ15፥4
120፥1 2ሳሙ22፥7፤መዝ18፥6፤118፥5
120፥2 መዝ31፥18፤52፥4 120፥4 ዘዳ32፥23
120፥5 ዘፍ25፥13፤ኤር2፥10

119፥163 *እጠላለሁ፤* የቍ53 ማብ ይመ። *ሐሰትን፤* ወይም "መንገዳቸው አታላይ" የሆነ ማለት ነው (ቍ29 እና ማብ ይመ)።

119፥164 *ሰባት፤* ፍጹምነትን የሚያመለክት ቃል ነው፤ መዝሙረኛው እግዚአብሔርን ቀኑን ሙሉ ሲያመሰግነውና ሲያወድሰው ይውላል፤ ያድራል።

119፥165 *ብዙ ሰላም፤* የሚያሰጋ ነገር የሌለበት ፍጹም አስተማማኝና ዋስትና ያለው ማለት ነው።

*119፥169-176፤* የቍ145-152 ማብ ይመ።

119፥171 *ምስጋናን አፈለቁ፤* ታድገኸኛልና ዘወትር አመሰግንሃለሁ ማለቱ ነው።

119፥172 *የጽድቅ፤* የቍ7 ማብ ይመ።

*119፥174-176፤* የመዝሙሩ መደምደሚያ ነው።

119፥176 *ተቅበዘበዝሁ፤* ኢሳ53፥6 ይመ። መዝሙረኛው ለእግዚአብሔር ሕግ ለመገዛት ካለው ጽኑ ፍላጎት የተነሣ፣ ደግሞ ደጋግሞ በሐሰተኛ (በአታላይ) መንገድ እንደ ጠፋም በግ የባዘነ መሆኑንና በሰማያዊው እረኛ ተፈልጎ መገኘትና ወደ እግዚአብሔርም መመለስ እንዳለበት በግልጽ ይናገራል። የእግዚአብሔርን ሕግ የሕይወቱ መመሪያና ለሕይወቱም እንደ ዕንቍ ለቈጠረው ሰው የዚህ መዝሙር የመጨረሻ ቃል ንስሓና ጸሎት ነው።

*መዝ120፤* ከሐሰተኛ ከሳሾች እግዚአብሔር እንዲታደገው ያቀረበው ጸሎት ነው። ቍጥር 7 የመዝሙሩ ባለቤት ንጉሥ እንደ ሆነ ይጠቍማል፤ እንዲህ ከሆነ የንጉሡ ከሳሾች ንጉሡን በሕዝቡ ፊት ለማሳጣት የፈለጉ ወይም ባዕዳን ነገሥታት በንጉሡ ላይ ጥርጣሬ እንዲያድርባቸው ለማድረግ ተንኰል የሸረቡ ይመስላል። ነገር ግን "ጦርነት" የተለዋዋጭ ዘይቤ ይዘት አለው የምንል ከሆነ መዝሙሩ በሐሜተኞች የተከበበ አንድ ሰው የተናገረው ነው ማለት ይቻላል።

120ርእስ፤ *መዓርግ፤* አንዳንድ ሰዎች ይህ ቃል የሚያመለክተው ወደ ቤተ መቅደሱ የሚያወጣውን ደረጃ ነው ይላሉ፤ ከዚህ የተነሣም መዝሙሩን "የደረጃ መዝሙር" ብለውታል፤ ይህ መዝሙር በቤተ መቅደሱ ውስጥ በተሰጥዎ መልክ (ምናልባት በዳስ በዓል ጊዜ) የሚዘመር ነው። ብዙዎች እንደሚናገሩት ግን ይህ ሐረግ ("የደረጃ መዝሙር") የሚያመለክተው፣ ተሳላሚዎች በየዓመቱ ወደ ኢየሩሳሌም ሲሄዱ የሚዘምሩት ነው (84፥5-7፤ ዘፀ 23፥14-17፤ ዘዳ16፥6፤ ሚክ4፥2፤ ዘካ14፥6 ይመ) ይላሉ፤ ይህ አባባል ግን መዝሙሩ በቤተ መቅደሱ ውስጥ በተሰጥዎ መልክ የሚዘመር ነው የሚለውን ቁርሽ አያደርግም። ይህ ርእስ በመዝ121-134 ሁሉ ላይ የሚገኝ ርእስ ሲሆን መዝሙሩ በመጀመሪያ ሲጻፍ የነበረውን መሠረታዊ ዐላማ ሳይሆን ከምርኮ በኋላ የነበረውን ሁኔታ እንደሚያመለክት ምንም ጥርጥር የለውም፤ እንዲሁም ርእሱ ከመዝ 120-134 ድረስ ያሉት መዝሙሮች አሁን ያላቸውን መልክ የያዙት ከምርኮ በኋላ መሆኑን ያሳያል። ይህ መዝሙር ከመዝ 135-136 ጋር በአይሁድ የተሰጥዎ ዝማሬ ውስጥ "ታላቁ የሃሌ ሉያ መዝሙር" በመባል ይታወቃል (እንዲህ የሚል ስያሜ የተሰጠው "የግብፃውያን ሃሌ ሉያ መዝሙር" ከሚለው ለመለየት ነው፤ የመዝ113 መግቢያ ይመ)። ይህን መዝሙር የመዝ 84 መንፈስ ከብቦታል (መዝ42-43 ይመ)።

120፥2 *ከሐሰተኛ ከንፈርና ከአታላይ ምላስም፤* የ5፥9 ማብ ይመ።

*120፥3-4፤* እግዚአብሔር ጣልቃ እንደሚገባ የሚገልጽ ማረጋገጫ ነው (6፥8-10 እና የ3፥8 ማብ ይመ)።

120፥3 *ከዚህስ የባሰ፤* የተለመደውን የመሐላ ቃል የሚያስታውስ ሲሆን (1ሳሙ3፥17 እና ማብ ይመ)፣ ይህም እግዚአብሔር በሕዝቡ ጠላቶች ላይ ፍርዱን እንደሚያመጣ በመዝሙረኛው በኩል በእርግጠኝነት ይናገራል።

120፥4 *በተሳለ ... ቀስት፤* ምላስ እንደ ሹል ቀስት ሁሉ የሚወጋ (ምሳ25፥18፤ ኤር9፥8 ይመ፤ እንዲሁም 57፥4፤ 64፥3 ይመ)፤ እንደ እሳት የሚፈጅ (ምሳ16፥27፤ ያዕ3፥6 ይመ) እንደ ሆነ ሁሉ የእግዚአብሔርም ፍርድ ልክ እንደዚሁ ነው (7፥11-13፤ 11፥6፤ 64፥7 ይመ)። ለተፈጸመ በደል ተገቢ ቅጣት እንደሚሰጥ በ63፥9-10፤ 64፥7-8 እና ማብ ይመ። *በግራር፤* በበረሓ የሚበቅል ሲሆን አንዳንድ ጊዜ እንደ ጥላ ያገለግላል።

*120፥5-7፤* በጠላቶቹ መካከል ለረጅም ጊዜ በመቀመጡ የተሰማውን ሐዘን የገለጸበት ክፍል ነው።

120፥5 *በሜሼክ ... በቄዳር፤* የመጀመሪያው ተከል በመካከለኛው ትንሹ እስያ የሚገኝ ሲሆን (የዘፍ10፥2 ማብ ይመ)፣ ሁለተኛው ደግሞ በዐረብ አገር ይገኛል (የኢሳ21፥16 ማብ ይመ)። መዝሙረኛው ራሱን የሚመለከተው በሐሜተኞችና በአምላክ የለሾች እንደ ተከበበ አድርጎ ነው።

## መዝሙር 121

### የእስራኤል ጠባቂ

*መዝሙረ መዓርግ*

[1]ዐይኖቼን ወደ ተራሮች አነሣሁ፤
ረድኤቴ ከወዴት ይመጣል?
[2]ረድኤቴ ሰማይንና ምድርን ከፈጠረ፣
ከ*እግዚአብሔር* ዘንድ ይመጣል።

[3]እግርህ እንዲሸራተት አይፈቅድም፤
የሚጠብቅህም አይተኛም።
[4]እነሆ፤ እስራኤልን የሚጠብቅ፣
አይተኛም፤ አያንቀላፋምም።

[5]*እግዚአብሔር* ይጠብቅሃል፤
*እግዚአብሔር* በቀኝህ በኩል ይከልልሃል።
[6]ፀሓይ በቀን አያቃጥልህም፤
ጨረቃም በሌሊት ጉዳት አታመጣብህም።

[7]*እግዚአብሔር* ከክፉ ሁሉ ይጠብቅሃል፤
ነፍስህንም ይንከባከባታል።
[8]*እግዚአብሔር* ከአሁን ጀምሮ እስከ ዘላለም፣
መውጣትህንና መግባትህን ይጠብቃል።

## መዝሙር 122

### ኢየሩሳሌም እልል በዪ!

*የዳዊት መዝሙረ መዓርግ*

[1]“ወደ *እግዚአብሔር* ቤት እንሂድ”
ባሉኝ ጊዜ፣
ደስ አለኝ።
[2]ኢየሩሳሌም ሆይ፤
እግሮቻችን ከደጆችሽ ውስጥ ቆመዋል።
[3]ኢየሩሳሌም እጅግ እንደ ተጠጋጋች፣
ከተማ ሆና ተሠርታለች።
[4]ለእስራኤል በተሰጠው *ሥርዐት* መሠረት፣
የ*እግዚአብሔርን* ስም ለማመስገን፣
የ*እግዚአብሔር* ነገዶች፣
ወደዚያ ይመጣሉ።
[5]በዚያም የፍርድ ዙፋኖች የሆኑት፣
የዳዊት ቤት ዙፋኖች ተዘርግተዋል።

[6]እንዲህ ብላችሁ ለኢየሩሳሌም ሰላም

121፥2 ዘፍ1፥1፤ መዝ104፥5
121፥4 መዝ127፥1
121፥5 መዝ1፥6
121፥6 ኢሳ49፥10
121፥7 መዝ9፥9
121፥8 ዘዳ28፥6
122፥6 መዝ26፥8

---

***መዝ121፤*** የኑዛዜና የዋስትና ቃለ ምልልስ ነው (ይህ ምናልባት የተሰጥዎ ዜማ ሊሆን ይችላል)። መዝሙሩ የተሳላሚዎች ዜማ በመሆኑ ለምን አገልግሎት እንደሚውል ከዚሁ መረዳት ይቻላል። ቃለ ምልልሱ አንድ ሰው ከራሱ ጋር ያደረገው (ከመዝ 42-43 አዝማቾች ጋር ያነጻጽሩ) ይሁን ወይም በጕዞ ላይ ያሉ ተሳላሚዎች እርስ በርስ ያደረጉት ይሁን ይህን ያህል የጐላ ልዩነት አያመጣም፤ ምክንያቱም ሁለቱም ወገኖች ተመሳሳይ እምነት አላቸው። በመዝሙሩ ውስጥ የተነገሩት የማጽናኛ ቃሎች (መዝ33 ይመ) ወደ ኢየሩሳሌም ለሚሄዱ ተሳላሚዎችም ሆነ ወደ “ክብሩ” ለሚገቡ ታማኝ የሕይወት ተሳላሚዎች ተገቢ ቃሎች ናቸው (የ49፥15፤ የ73፥24 ማብ ይመ)። መዝሙሩ በአራት ቤት የተዋቀረ ሲሆን እያንዳንዱ ቤት የራሱ የሆነ መግቢያ ስንኝ አለው፤ “እግዚአብሔር” እና “ይጠብቅሃል” የሚሉት ቃላት ቍልፍ ቃላት ሲሆኑ አምስት አምስት ጊዜ ተወሥተዋል።

121 *ርእስ፤* የመዝ120 ማብ ይመ።

*121፥1-2፤* በእግዚአብሔር ላይ ያለውን መታመን በግልጽ የተናገረበት ክፍል ነው።

121፥1 *ተራሮች፤* በኢየሩሳሌም ዙሪያ የሚገኙ ኩረብታዎች ሲሆን ከእነዚህም ውስጥ አንዱ ወይም የጽዮን ተራራ ነው (125፥2)፤ ወይም ደግሞ ብዙው ቍጥር የሚያመለክተው (በዕብራይስጡ በ87፥1፤ በ133፥3 ላይ እንደ ተጠቀሰው) ግርማን ከሆነ መዝሙረኛው የተናገረው ስለ ጽዮን ተራራ ነው።

121፥2 *ሰማይንና ምድርን ከፈጠረ፤* የፍጥረት ሁሉ ንጉሥ (124፥8፤134፥3 ይመ። እንዲሁም 33፥6፤ 89፥11-13፤ 96፥4-5፤ 104፥2-9፤ 136፥4-9 ይመ) የሆነውን አንዱን እውነተኛ አምላክ ነው።

*121፥3-4፤* እስራኤልን ስለሚጠብቀው የማይተኛ አምላክ የተነገረ ቃል ነው።

121፥3 *እግርህ እንዲንሸራተት፤* መንገዱ የሚያዳልጥ መንገድ ቢሆንም እንኳ ከቶ እንድትወድቅ አያደርግም ማለት ነው። *አይተኛም፤* እንደ አሕዛብ አምላክ እንደ በዓል የእስራኤል አምላክ አይተኛም (1ነገ18፥27 ይመ)።

121፥4 *እስራኤልን የሚጠብቅ፤* ይህ የእስራኤል ጠባቂ የፍጥረት ሁሉ ጌታ፣ እስራኤልን ተግቶ የሚጠብቅና ታማኞች ዘወትር የሚተማመኑበት ነው።

*121፥5-6፤* እግዚአብሔር ለሕዝቡ የማያቋርጥ ጥበቃ እንደሚያደርግ የሚያረጋግጥ ቃል ነው።

121፥5 *ይከልልሃል፤* 91፥1 (“መጠጊያ”) የሚለውንና የ17፥8 ማብ ይመ። *በቀኝህ በኩል፤* 16፥8 እና ማብ ይመ።

121፥6 *ፀሓይ ... ጨረቃም፤* እዚህ ላይ “ከለላ” ከሚለው ተለዋጭ ዘይቤ ጋር ይስማማል፤ እነዚህ ቃላት ቀንም ሆነ ሌሊት ለሚያስጨንቁና ለሚያስፈሩ ነገሮች እንደ ምሳሌ ሆነው ያገለግላሉ (ኢሳ4፥6፤ 25፥4-5፤ 49፥10፤ ዮና4፥8 ይመ)።

*121፥7-8፤* መላ ሕይወቱን እንደሚጠብቅለት የተነገረ ማረጋገጫ ነው።

121፥8 *መውጣትህንና መግባትህን፤* ባጭሩ እንቅስቃሴህን ሁሉ ማለት ነው።

***መዝ122፤*** ስለ ኢየሩሳሌም የተነገረ የደስታ መዝሙር ነው (መዝ42-43፤ 46፤ 48፤ 84፤ 87፤137 እና መግቢያዎቻቸውን ይመ)። መዝሙሩ ወደ ኢየሩሳሌም በሚጓዙ ተሳላሚዎች (ምናልባት በየዓመቱ ከሚከበሩ ሦስት በዓላት በአንዱ ላይ የሚዘመር ነው፤ ዘዳ16፥16) የሚዘመር ነው፤ መዝሙረኛው በከተማዋ የተሰማውን ጥልቅ ደስታና ስለ ከተማዋ ደኅንነት ያቀረበው ጸሎት ይህንኑ ይገልጻል። ይህ መዝሙር ሦስተኛ የተሳላሚዎች መዝሙር እንደ መሆኑ መጠን (የመዝ120 መግቢያ ይመ) ከመዝ132 ጋር የሚጋራው በርካታ ዐበይት ፍሬ ሐሳቦች አሉት። በአወቃቀር ረገድ ሲታይ መዝሙሩ የተቀነበበው “የእግዚአብሔር ቤት” (ቍ1፡9) በሚለው ሐረግ ነው።

122 *ርእስ፤ የምዕራግ፤* የመዝ120 ማብ ይመ። *የዳዊት፤* ቃሉ በጥንት ጽሑፎች ላይ አይገኝም፤ ምናልባት ከጊዜ በኋላ የተጨመረ ሳይሆን አይቀርም (የቍ1 ማብ ይመ)።

*122፥1-2፤* መዝሙረኛው ወደ ኢየሩሳሌም ከሚሄዱ ተሳላሚዎች ጋር አብሮ ለመሄድ በመታደሉ ደስታውን ይገልጻል።

122፥1 *ወደ እግዚአብሔር ቤት፤* ቤተ መቅደሱ ነው (2ሳሙ7፥5፡13፤ 1ነገ5፥3፡5 “ቤተ መቅደስ” 8፥10 “ቤተመቅደስ”) ከ1ነገ3፥4፤ 8፥1-11 አንጻር ሲታይ ቤተ መቅደሱ አገልግሎቱን በይፋ ከመጀመሩ በፊት ኢየሩሳሌምም ተሳላሚዎች የሚሄዱባት ከተማ ነበረች ለማለት የሚያሳፍር ነገር የለም።

122፥2 *ከደጆችሽ፤* የከተማዪቱ ቅጥር በሮች ናቸው።

*122፥3-5፤* ኢየሩሳሌም ለታማኝ ሰዎች ያላትን ቦታ የሚገልጽ ክፍል ነው።

122፥3 *ተጠጋጋች፤* መኖሪያ ቤቶቿ እርስ በርስ ተያይዘው የተሠሩ መሆናቸውን የሚያመለክት ቃል ሊሆን ይችላል (መዝ 48 ይመ)። ወይም ደግሞ “እንደ አንድ ወጥ አድርገህ አያይዘው” በማለት በዘፀ26፥11 ላይ ስለ ምስክሩ ድንኳን አሠራር የተጻፈውን የሚያስታውስ ቃል ሊሆን ይችላል። ይህ አባባል ትክክል ሆኖ ከተገኘ ኢየሩሳሌም የእግዚአብሔር ማደሪያ እንደ ሆነች ተቈጥሮ ክብረ በዓል ሊደረግባት ይገባል (የ9፥11 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ4፥5 ይመ)።

122፥4 *ለማመስገን፤* ውዳሴ የሚቀርበው እግዚአብሔር በእስራኤል መካከል ስላደረገው የማዳን ሥራና በሕዝቦች ላይ ስላፈሰሰው በረከት ነው። *ስም፤* የ5፥11 ማብ ይመ። *ለእስራኤል በተሰጠው ሥርዐት፤* 81፥3-5፤ ዘዳ16፥1-17 ይመ።

122፥5 *በዚያም ... የዳዊት ቤት ዙፋኖች፤* ኢየሩሳሌም የእግዚአብሔር ከተማና እርሱ ለመረጠው ሥርወ መንግሥት መናገሻ ናት፤ እግዚአብሔር ሕዝቦችን የሚያስተዳድረው ከዚህ ሥርወ መንግሥት በሚወጣው ንጉሥ ነው (2፥2፡6-7፤ 89፥3-4፡19-37፤ 110፤ 2ሳሙ7፥8-16 እና ማብ ይመ) ምንም እንኳ አሁን በመሲሓዊ ተስፋ ውስጥ ብትሆንም ከምርኮ በኋላ የዳዊት ከተማ እንደ ሆነች ቀጥላለች።

*122፥6-9፤* ስለ ኢየሩሳሌም ሰላም የቀረበ ጸሎት ነው።

*122፥6፤* በዕብራይስጡ ቅጅ ላይ “ጸሎት”፣ “ሰላም”፣ “ኢየሩሳሌም” እና “ዋትና ያላት” የሚሉት ቃላት ማራኪ በሆነ መንገድ እርስ በርስ ተሳስረዋል። *ሰላም፤* ቍ7-8 ይመ። ይህ

ጸልዩ፤
"የሚወዱሽ ይለምልሙ፤
[7]በቅጥርሽ ውስጥ ሰላም ይሁን፤
በምሽግሽም ውስጥ መረጋጋት
ይስፈን"::
[8]ስለ ወንድሞቼና ስለ ባልንጀሮቼ፣
"በውስጥሽ ሰላም ይስፈን" እላለሁ::
[9]ስለ ስምባካችን ስለ እግዚአብሔር ቤት፣
በጎነትሽን እሻለሁ::

## መዝሙር 123
### የተጨነቀ ሰው ጸሎት
*መዝሙረ መዓርግ*

[1]በሰማይ ዙፋን ላይ የተቀመጥህ ሆይ፤
ዐይኖቼን ወደ አንተ አነሣለሁ::
[2]የባሪያዎች ዐይን ወደ ጌታቸው እጅ፣
የባሪያይቱም ዐይን ወደ እመቤቷ
እጅ እንደሚመለከት፣
ምሕረት እስከሚያደርግልን ድረስ፣
የእኛም ዐይኖች ወደ ስምባካችን ወደ
እግዚአብሔር ይመለከታሉ::
[3]እግዚአብሔር ሆይ፤ ንቀት
በዝቶብናልና፣
ማረን፣ እባክህ ማረን::
[4]ነፍሳችን የቅንጡዎች ስድብ፣
የትዕቢተኞችም ንቀት እጅግ በዝቶባታል::

122፥7 1ሳሙ25፥6፤መዝ48፥3
122፥9 መዝ128፥5
123፥1 መዝ68፥5፤ ኢሳ6፥1፤63፥15
123፥2 መዝ25፥15
124፥1 መዝ129፥1
124፥4 መዝ81፥4፤88፥17
124፥7 መዝ25፥15፤91፥3
124፥8 ዘፍ1፥1፤ 1ሳሙ17፥45፤መዝ 115፥15፤121፥2፤134፥3
125፥1 መዝ46፥5፤48፥2-5፤12፤ኢሳ 33፥20

## መዝሙር 124
### የእስራኤል አዳኝ
*የዳዊት መዝሙረ መዓርግ*

[1]እስራኤል እንዲህ ይበል:-
"እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ባይሆን ኖሮ፣
[2]ሰዎች በእኛ ላይ በተነሡ ጊዜ፣
እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ባይሆን ኖሮ፣
[3]ቍጣቸው በላያችን በነደደ ጊዜ፣
በቁመናችን በዋጡን ነበር፤
[4]ጐርፍ ባጥለቀለቀን፣
ፈረሰኛው ውሃ ባሰጠመን፣
[5]ደራሽ ውሃም
ጠራርጎ በወሰደን ነበር::
[6]በጥርሳቸው ከመዘንጠል የጠበቀን፣
እግዚአብሔር ይባረክ::
[7]ነፍሳችን እንደ ወፍ፣
ከአዳኝ ወጥመድ አመለጠች፤
ወጥመዱ ተሰበረ፤
እኛም አመለጥን::
[8]የሰማይና የምድር ፈጣሪ፣
የእግዚአብሔር ስም ረዳታችን ነው::

## መዝሙር 125
### እግዚአብሔር የሚታመኑበትን ይጠብቃል
*መዝሙረ መዓርግ*

[1]*በእግዚአብሔር የሚታመኑ*፣
ሳትናወጥ ለዘላለም እንደምትኖር እንደ

---

ቃል ዋስትናንና ብልጽግናን ይይዛል:: አንቺንም የሚወዱ፤ ይህ ቺን ከተማ የሚወዱት መዝሙረኛው፣ በቍ1:8 ላይ የተጠቀሱትና ኢየሩሳሌምን የሚወዱ ሁሉ ናቸው፤ ምክንያቱም ለጌታና እርሱ ለመረጠው ንጉሥ የተገዙ ናቸው:: ይህም እንደ እግዚአ ብሔር ሕዝብ በአንድነት የሚያመልኩትን፣ አብረው የሚጸል ዩትንና እርስ በርስ የሚተሳሰቡትን ያካትታል (መዝ133 ይመ)::

122፥7 *በቅጥርሽ ... በምሽግሽም፤* 48፥13 ይመ ("ግን ቦቿን ... ምሽጎቿን")::

*122፥8-9 ስለ ... ስለ፤* ኢየሩሳሌም፣ እግዚአብሔርና ሕዝቡ ልዩ በሆነ አንድነት የሚገኙበት ከተማ በመሆኗ መዝሙ ረኛው ሰላም የሰፈነባት ከተማ እንድትሆን ከልብ ይመኛል::

*መዝ123፤* እግዚአብሔር ምሕረቱን እንዲያወርድላቸውና የእብሪተኞችን ንቀትና ድፍረት ዝም እንዲያሰኝላቸው ትሑ ታን የእግዚአብሔር ሕዝብ ያቀረቡት ጸሎት ነው:: የመዝ124 መግቢያ ይመ:: ባወቃቀር ደረጃ ሲታይ መዝሙሩ ባለ አንድ ቍጥር መግቢያና ባለ ሁለት ቤት ስንኝ ያለው ነው፤ ባለ ሁለት ቤት ስንኞች የየራሳቸውን ዋና ሐሳብ አጉልብተዋል::

123፥1 *በሰማይ ዙፋን ላይ፤* ዙፋኑ በሰማይ የሆነው አም ላክ ምድራዊ ዙፋኑን በጽዮን ተራራ ላይ በሚገኘው ቤተ መቅደስ ውስጥ አድርጎታል (122፥5 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 2፥4፡9:11፤ 11፥4፤ 80፥1፤ 99፥1፤ 113፥5፤ 132፥14 ይመ)::

123፥2 *የባሪያዎች ... የባሪያይቱም፤* ንጽጽር ነው፤ በዚህ ዐይነት ታማኝ የእግዚአብሔር ሕዝቦች (ወንዶችም ሆኑ ሴቶች) የሚ ታመኑት በእግዚአብሔር ብቻ እንደ ሆነ ዐውቀው ራሳቸ ውን በትሕትና ለእርሱ እንደሚሰጡ ተገልጿል::

123፥4 *የትዕቢተኞችን ... የእብሪተኞችን፤* በራሳቸው ብልጠትና ጉልበት የሚኖሩ ሰዎች (የ10፥2-11፤ 31፥23 ማብ ይመ) በእግዚአብሔር የሚታመኑትን ሰዎች ከቶኛ ይንቃሉ፤ በተለይ ደግሞ በእግዚአብሔር የሚታመኑ ሰዎች መከራ ሲደር ስባቸው ወይም ብልጽግና ፊቱን ሲያዞርባቸው ንቀታቸውን በይፋ ያሳያሉ::

*መዝ124፤* እግዚአብሔር ከኀይለኛ ጠላቷ እጅ ስለታደጋት እስራኤል ያቀረበችለት ውዳሴ ነው:: ከመዝ123 ተከትሎ መጻፉ ትክክል ነው:: ከቍ1-5 ያለው ክፍል የሚናገረው ሌዋዊ ሲሆን ከቍ6-8 ያለውን ደግሞ ሕዝቡ በተሰጥዎ መልክ ይመልሳል:: እንደ መዝ129 ሁሉ ይህም መዝሙር በሁለት አንጓ ይከፈላል::

124 ርእስ፤ *የምዕራግ፤* የመዝ120 ማብ ይመ:: *የዳዊት፤* ሁሉም ጥንታዊ ቅጆች ይህን ቃል አይጠቅሱም፤ የመዝሙሩ ቋንቋና ዐቢይ ሐሳብ እንደሚያመለክቱት መዝሙሩ የተጻፈው ከምርኮ በኋላ ነው (የመዝ122 ርእስ ማብ ይመ):: መዝሙሩ ለዳዊት የተሰጠው የመዝ18፤ 69 ሐሳቦችን ስለሚያስ ተጋባ ሊሆን ይችላል::

*124፥1-5፤* ከመጥፋት ያዳናት እግዚአብሔር እንጂ ሌላ አለመሆኑን እስራኤል ልታውቅ ይገባል (20፥7፤94፥17 ይመ)::

124፥2 *ሰዎች በተነሡ ጊዜ፤* ትዕቢተኞችና እብሪተኞች ሰዎች (መዝ123፥4) ሊያጠቋት ቢነሱም እግዚአብሔር ግን የእስ ራኤል ረዳት ነው (ቍ8)::

124፥3 *በዋጡን ነበር፤* እንደ ሞት (የ49፥14 ማብ ይመ)፤ ይሁን እንጂ 69፥15 ይመ::

124፥4-5 *ጐርፍ ... ፈረሰኛው ውሃ ... ደራሽ ውሃም፤* መዝ18፥16 ይመ፤ እንዲሁም 32፥6፤ 69፥1-2 እና ማብ ይመ::

*124፥6-8፤* እግዚአብሔር ላላያቸው ማዳን የቀረበ ምስጋና ነው፤ ምስጋናው የቀረበው ምስል ከሳች በሆነ ቋንቋ ነው::

124፥6 *በጥርሳቸው ከመዘንጠል፤* የዱር አውሬዎች ያገኙትን ሁሉ ዘነጣጥለው እንደሚጥሉ ማለት ነው (የ7፥2 ማብ ይመ)::

124፥7 *እንደ ወፍ፣ ከአዳኝ ወጥመድ አመለጠች፤* እስራ ኤላውያን ከባቢሎን ምርኮ እንዴት ነጻ እንደወጡ የሚገ ልጽ ውብ አነጋገር ነው::

*124፥8፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ አለኝታ እግዚአብሔር ብቻ መሆኑን የሚገልጽ ቃል ነው (121፥2 እና ማብ ይመ)::

*መዝ125፤* የእስራኤል ሰላም በምስክርነት፣ በጸሎትና በቡ ራኬ ተነገረ:: መዝሙሩ የተጻፈው ከምርኮ በኋላ ሲሆን አንድ ሌዋዊ በተሰጥዎ ጊዜ የተናገረው ሳይሆን አይቀርም::

125 *ርእስ፤* የመዝ120 ማብ ይመ::

*125፥1-2፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ ታላቅ ጥበቃ እንደሚደ ረግለት የሚያውጅ ክፍል ነው::

125፥1 *በእግዚአብሔር የሚታመኑ፤* እነዚህ ሰዎች የእግዚ አብሔር "ሕዝብ" (ቍ2) "ጻድቃን" (ቍ3) "ቸሮች" እና "ቅን ልብ ያላቸው" (ቍ4) ናቸው:: ስለ "ጻድቃን" ተጨማሪ ገለጻ ለማግኘት 34፥8-14 እና ማብ ይመ:: *እንደ ጽዮን ተራራ፤* ጽኑ መታመኛቸው ማን እንደ ሆነ የሚያሳይ ነው (መዝ46፤ 48 ይመ)::

ጽዮን ተራራ ናቸው::
²ተራሮች ኢየሩሳሌምን እንደ ከበቧት፣
ከአሁን ጀምሮ ለዘላለም፣
እግዚአብሔር በሕዝቡ ዙሪያ ነው::
³ጻድቃን እጃቸውን፣
ለክፋት እንዳያነሡ፣
የክፉዎች በትር፣
ለጻድቃን በተመደበች ምድር ላይ
አያርፍም::

⁴እግዚአብሔር ሆይ፤ መልካም ለሆኑ፣
ልባቸውም ለቀና መልካም አድርግ::
⁵ወደ ጠማማ መንገዳቸው የሚመለሱትን
ግን፣
እግዚአብሔር ከክፉ አድራጊዎች ጋር
ያስወግዳቸዋል::

በእስራኤል ላይ ሰላም ይውረድ::

## መዝሙር 126

### የስደት ተመላሾች መዝሙር

መዝሙረ መዓርግ

¹እግዚአብሔር የጽዮንን ምርኮ[ሖ] በመለስ[ፐ]
ጊዜ፣
ሕልም እንጂ እውን አልመሰለንም::
²በዚያን ጊዜ አፋችን በሣቅ፣
እንደበታችንም በእልልታ ተሞላ፤
በዚያን ጊዜም በሕዝቦች መካከል፣
"እግዚአብሔር ታላቅ ነገር
አደረገላቸው" ተባለ::
³እግዚአብሔር ታላቅ ነገር አደረገልን፤
እኛም ደስ አለን::

⁴እግዚአብሔር ሆይ፤ በነጌብ እንዳሉ ጅረቶች፣
ምርኳችንን መልስ::[ሀ]
⁵በእንባ የሚዘሩ፣
በእልልታ ያጭዳሉ::
⁶ዘር ቋጥረው፣
እያለቀሱ የተሰማሩ፣
ነዶአቸውን ተሸክመው፣
እልል እያሉ ይመለሳሉ::

## መዝሙር 127

### በእግዚአብሔር መታመን

የሰሎሞን መዝሙረ መዓርግ

¹እግዚአብሔር ቤትን ካልሠራ፣
ሠራተኞች በከንቱ ይደክማሉ፤
እግዚአብሔር ከተማን ካልጠበቀ፣
ጠባቂ በከንቱ ይተጋል::

125፥2 1ዜና21፥15፤ መዝ32፥10፤ዘካ2፥4-5
125፥3 1ሳሙ24፥10፤ አስ4፥11፤መዝ89፥22፤ምሳ22፥8፤ኢሳ 13፥11፤14፥5
125፥4 መዝ36፥10፤119፥65
125፥5 ኢዮ23፥11፤ መዝ92፥7፤128፥6፤ ምሳ2፥15፤17፥6፤ ኢሳ59፥8፤ገላ6፥16
126፥1 ዕዝ1፥1-3፤ መዝ85፥1፤ሆሴ6፥11
126፥2 ዘፍ21፥6፤ ዘዳ10፥21፤ኢዮ8፥21፤ መዝ65፥8፤71፥19፤ ሉቃ1፥49
126፥3 መዝ9፥2፤ 16፥11፤106፥21፤ኢል 2፥21፡26
126፥4 ዘዳ30፥3፤ መዝ107፥35፤ኢሳ 43፥19፤51፥3
126፥5 መዝ6፥6፤ 16፥11፤20፥5፤23፥6፤ 80፥5፤ኢሳ35፥10፤ 51፥11፤60፥15፤61፥7 ፤ኤር31፥6-7፡12፤ 50፥4፤ገላ6፥9
126፥6 ዘኍ25፥6፤ መዝ30፥5
127፥1 መዝ78፥69 ፤121፥4

[ሖ]1 ወይም እግዚአብሔር ሀብቷን ይመልሳል::
[ፐ]1 ወይም የሰዎቿ ጤንነት ይታደሳል::
[ሀ]4 ወይም ሀብታችንን መልስ

125፥2 *ተራሮች ኢየሩሳሌምን እንደ ከበቧት፤* ምንም እንኳ ኢየሩሳሌም ዙሪያዋን በቀለበት ተራራ የተከበበች ባተሆንም ከተማዋ የተመሠረተችው የብሉይ ኪዳን ጸሐፊዎች ተራራማ ክልል ብለው በሚጠሩት ስፍራ ነው:: እግዚአብሔርም ሕዝቡን አሁንም ይከባቸዋል፤ እንዳይናወጡ፣ እንዳይበታተኑና እንዳይፈራርሱ ዙሪያቸውን ይከባቸዋል (2ነገ6፥17፤ ዘካ2፥5 ይመ)::

*125፥3፤* ክፉ ገዦች በተግባራቸውም ሆነ በጭቈናቸው ጻድቃንን ለመበከል ይሞክራሉ፤ ይሁን እንጂ እግዚአብሔር ሕዝቡን ይህን ከመሰለው አስከፊ ብክላ ይጠብቃል:: *የክፉዎች በትረ መንግሥት፤* ምናልባት የፋርስን ገዦችና (ነህ9፥36-37 ይመ) ነህምያ አጥብቆ የተቃወማቸውን ታናናሽ ሹማምንት ሳይሆን አይቀርም (ነህ2፥19፤ 4፥1-3፡7-8፤6፥1-14፡17-19፤ 13፥7-8፡28 ይመ):: *ለጻድቃን በተመደበላቸው ምድር፤* የተስፋዪቱን ምድር ነው (78፥5)::

*125፥4-5፤* ለእያንዳንዱ እንደ ሥራው መክፈል የእግዚአብሔር ባሕርይ ነው (18፥25-27 ይመ)፤ ስለዚህ መዝሙረኛው ጸሎቱ እንደሚሰማና (ቍ 4) ለጸሎቱም መልስ እንዲያገኝ እርግጠኛ ነው (ቍ5)::

125፥4 *ልባቸውም፤* የ4፥7 ማብ ይመ::

125፥5 *በእስራኤል ላይ ሰላም ይውረድ፤* ምናልባት እጥር ምጥን ባለ መልኩ የቀረበ የካህናት ቡራኬ ነው (ዘኍ6፥24-26)::

*መዝ126፤* ስለ ጽዮን እንደ ገና መታደስ የተዜመ የደስታ መዝሙር ነው:: መዝሙሩ የተጻፈው ከባቢሎን ምርኮ ለተመለሱት ሰዎች (ዕዝራንና ነህምያን ይመ) አይደለም የሚባል ከሆነ (የምርኮው ቦታ አልተጠቀሰም) መዝሙሩ እንደ ገና የታደሰን ወይም የተጐበኘን አንድ ኅብረተሰብ ደስታ ለማስተጋባት አገልግሎአል (ከመዝ42-43፤ 84፤ 137 ጋር ያነጻጽሩ):: መዝሙሩ እያንዳንዳቸው አራት አራት ስንኞች ባሏቸው ሁለት አንጓዎች የተከፈለ ሲሆን የስንኞቹ መጀመሪያ መስመር የጋራ ዐቢይ ሐሳብ አላቸው:: የስንኞቹ ዐቢይ ሐሳብ ተያያዥነት እንዳላቸው የሚያሳዩ ሌሎች ቃሎች አሉ ("እግዚአብሔር"፣ "የደስታ መዝሙር"፣ "ተሸክመው"):: የመጀመሪያው አንጓ የተቀነበበው የእግዚአብሔር ሥራ በሚያወሣው ቃል ሲሆን (ቍ1፡3) ቍጥር 2 ደግሞ ሐሳቡን የበለጠ ያብራራል::

126፥1 *ርእስ፤* የመዝ120 ርእስ ማብ ይመ::

*126፥1-3፤* ከምርኮ በመመለሳቸው የተሰማቸውን ደስታ የሚገልጽ ክፍል ነው::

126፥1 *ምርኮ ... በመለስ ጊዜ፤* የቍ4 ማብ ይመ:: *ሕልም እንጂ፤* የተደረገላቸው ድንቅ ሥራ እጅግ የሚያስገርም ከመሆኑ የተነሣ ለእነርሱ እንደ ተደረገ ለማመን ተቸገሩ:: በተስፋ በጕጕት ሲጠብቁት የነበረው ነገር እንዲሁ ሕልም ብቻ ሆኖ የሚቀር እንጂ እውን ሆኖ እናየዋለን ብለው አላሰቡም ነበር::

*126፥2፤* እግዚአብሔር በመካከላቸው ያደረገው ነገር ሁለት ውጤቶችን አስከትሎአል፤ አንደኛው ከምርኮ የተመለሱት የተሰማቸው ሐሴት ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ እግዚአብሔር በአሕዛብ ዘንድ ያገኘው ክብር ነው (የ46፥10 ማብ ይመ)::

*126፥4-6፤* ከምርኮ የመመለሳቸው ጕዳይ ይፈፀም ዘንድ የቀረበ ጸሎት ነው::

126፥4 *ምርኮአችንን... መልስ፤* ከምርኮ አገር ሕዝቦቻችንን ፈጽሞ መልስ ወይም የቀድሞውን ዘመን ሰላምና ብልጽግና መልስልን ማለት ነው:: *በነጌብ ምድረ በዳ እንዳሉት ፈሳሾች፤* የክረምቱ ዝናብ መጥቶ እስኪሞላ ድረስ ክው ብለው የደረቁ ወንዞች ናቸው::

*126፥5-6፤* አሁን ያገኙትንና ወደፊት የሚያገኙትን ደስታ የሚገልጽ ምሳሌያዊ አነጋገር ነው:: *በእንባ ... እያለቀሱ፤* ዘር የሚዘሩ በሐዘንና በመከራ ታጅበው ቢዘሩም በመከር ጊዜ ሐሴት ያደርጋሉ:: ከዚህ ጋር የሚመሳሰል ምሳሌያዊ አነጋገር በ20፥5 ላይ ይመ::

*መዝ127፤* ስለ ቤትና ስለ ንብረት እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው የተናገረው የጥበብ ቃል ነው:: የመዝሙሩ ዐቢይ ሐሳብ ጊዜ የማይሽረውና የማይለውጠው አባባል ነው፤ መዝሙሩ ተሳላሚዎች ወደ ኢየሩሳሌም በመጓዝ ላይ ሳሉ ሕይወታቸው ከክፉ ነገር የምትጠበቀውና በረከት የምታገኘው በእነርሱ ጥረት ሳይሆን፣ ከእግ ዚአብሔር ቸርነት የተነሣ መሆኑን ያሳስባቸዋል (ዘዳ 28፥1-14 ይመ):: ሁለት ተመጣጣኝ አንጓዎች ሁለት የተለያዩ ነገር ግን የእርስ በርስ ዝምድና ያላቸውን ዐቢይ ሐሳቦች ተከትለው ቀርበዋል::

127ርእስ፤ *መዓርግ፤* የመዝ120 ርእስ ማብ ይመ:: *የሰሎሞን፤* የመዝሙሩ ጸሐፊ ሰሎሞን አይደለም የሚሉ ሰዎች ቢኖሩም (ሁሉም ጥንታዊ ቅጆች ሰሎሞን እንደ ሆነ አይናገሩም) አንዳንድ ሰዎች ግን የመዝሙሩ ጸሐፊ ሰሎሞን ነው ያሉበት ምክንያት ግልጽ ነው::

*127፥1-2፤* ለሰው መጠለያን፣ ሰላምንና የዕለት ምግብን የሚሰጥ እግዚአብሔር ነው::

127፥1 *ቤትን፤* የሰው መኖሪያ ነው:: *ሠራተኞች፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ድምፅ በቍ3 ላይ "ወንዶች ልጆች" የሚለውን ለመግለጽ ከገባው የዕብራይስጥ ቃል ድምፅ ጋር ተመሳሳይ ነው:: *ካልጠበቀ፤* 121፥3-8 ይመ:: *ከተማ፤* ጠላት አገርን በሚወርበት ጊዜ የኀይል ማእከል ወይም መሸሸጊያ ነው:: *ጠባቂ፤* 2ሳሙ13፥34፤18፥24-27፤ ማሕ3፥3፤ 5፥7 ይመ::

²የዕለት ጉርስ ለማግኘት በመጣር፣
ማልዳችሁ መነሣታችሁ፣
አምሽታችሁም መተኛታችሁ ከንቱ ነው፤
እርሱ ለሚወዳቸው እንቅልፍን ያድላልና።^
³እነሆ፤ ልጆች የእግዚአብሔር ስጦታ
ናቸው፤
የማሕፀንም ፍሬ ከቸርነቱ የሚገኝ ነው።
⁴በወጣትነት የተገኙ ወንዶች ልጆች፣
በጦረኛ እጅ እንዳሉ ፍላጻች ናቸው።
⁵ኰረጆዎቹ በእነዚህ የተሞሉ፣
የተባረከ ሰው ነው፤
ከጠላቶቻቸው ጋር በአደባባይ በሚሟ
ገቱበት ጊዜ፣
አይዋረዱም።

## መዝሙር 128
### የጻድቃን በረከት
መዝሙረ መዓርግ

¹እግዚአብሔርን የሚፈሩ ሁሉ፣
በመንገዱም የሚሄዱ የተባረኩ ናቸው።
²የድካምህን ፍሬ ትበላለህ፤
ትባረካለህ፤ ይሳካልሃልም።
³ሚስትህ በቤትህ፣
እንደሚያፈራ ወይን ናት፤
ወንዶች ልጆችህ በማእድህ ዙሪያ፣
እንደ ወይራ ተክል ናቸው።
⁴እነሆ፤ እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው፣
እንዲህ ይባረካል።
⁵እግዚአብሔር ከጽዮን ይባርክህ፤
በሕይወትህ ዘመን ሁሉ፣
የኢየሩሳሌምን ብልጽግና ያሳይህ፤
⁶የልጅ ልጅ ለማየትም ያብቃህ።
በእስራኤል ላይ ሰላም ይውረድ።

## መዝሙር 129
### በጽዮን ጠላቶች ላይ የቀረበ ጸሎት
መዝሙረ መዓርግ

¹እስራኤል እንዲህ ይበል፦
"ከልጅነቴ ጀምሮ ብዙ ጊዜ አስጨነቁኝ፤
²በእርግጥ ከልጅነቴ ጀምሮ ብዙ ጊዜ
አስጨነቁኝ፤
ዳሩ ግን ድል አላደረጉኝም።
³ዐራሾች ጀርባዬን ዐረሱት፤
ትልማቸውንም አስረዘሙት።"
⁴እግዚአብሔር ግን ጻድቅ ነው፤

^2 ወይም ተኝተው ሳሉ ምግብ ያዘጋጅላቸዋል።

127፥2 ዘፍ3፥17፤ ዘኍ6፥26፤ዘዳ33፥12፤ ኢዮ11፥18፤መክ2፥25
127፥3 ዘፍ1፥28
127፥4 መዝ112፥2 ፤127፥5፤ዘፍ23፥10፤ 24፥60፤መዝ128፥2-3
127፥5 ዘፍ23፥10፤ 24፥60፤መዝ128፥2-3
128፥1 መዝ103፥11 ፤112፥1፤119፥1-3
128፥2 ዘፍ39፥31 መዝ58፥11፤109፥11፤ ምሳ10፥22፤ኢሳ3፥10
128፥3 ዘፍ49፥22 ፤ኢዮ29፥5፤መዝ 52፥8፤144፥12
128፥4 መዝ1፥1፤ 112፥1
128፥5 መዝ20፥2፤ 122፥9
128፥6 ዘፍ48፥11፤ መዝ125፥5
129፥1 ዘፀ1፥13፤ መዝ88፥15፤124፥1
129፥2 ኤር1፥19፤ 15፥20፤20፥11፤ማቴ 16፥18
129፥4 ዘፀ9፥27፤ መዝ37፥9፤140፥5

127፥2 ... *እንቅልፍን ይሰጣል፤* መልካም ምርት የሚገ ኘው በግረትና በተረት ሳይሆን ከእግዚአብሔር የሚገኝ በረከት ውጤት ነው (ምሳ10፥22፤ ማቴ6፥25-34፤ 1ጴጥ5፥7 ይመ)። *ለሚወዳቸው፤* በተለይ ዘዳ33፥12፤ ኤር11፥15 ይመ።

*127፥3-5፤* ልጆች የእግዚአብሔር ስጦታዎች ናቸው፤ እን ዲሁም በእርሱ ዘንድ ሞገስ ማግኘታችንን የሚገልጹ ምልክቶች ናቸው።

127፥3 *ልጆች፤* የቍ1 ማብ ይመ። ልጆች የእግዚአብሔር ስጦታ እንጂ በሩካቤ ሥጋ የሚገኙ ብቻ አይደሉም (113፥9 እና ማብ፤ እንዲሁም ዘፍ30፥2 ይመ)። *ስጦታ፤* እዚህ ላይ ቃሉ የሚያመለክተው ስጦታን እንጂ ባለቤትነትን አይደለም። ይሁን እንጂ ቃሉ ከዚህም የላቀ መልእክት ሊኖረው ይችላል። በብሉይ ኪዳን ውስጥ እግዚአብሔር ለእስራኤላውያን የሰጠው "ርስት" የተስፋዪቱን ምድር ሲሆን (ዘኍ26፥53፤ ኢሱ11፥23፤ መሳ2፥6) ይህም ምድር እስራኤላውያን በእግዚአብሔር መንግሥት ውስጥ ያላቸው ድኑ "መኖሪያ" ነው (ኢሱ1፥13)። ነገር ግን ልጅ ከሌላ ቸው በምድሪቱ ውስጥ ርስት አይኖራቸውም (ዘኍ27፥8-11)፤ ስለዚህ ልጆች ትልቅ ስጦታ ናቸው ማለት ይቻላል። *በረከት ናቸው፤* እግዚአብሔር ታማኝ በመሆኑ በፊቱ ሞገስ ላገኙ ሁሉ የሚሰጠው በረከት ነው።

127፥5 *ከጠላቶቻቸው ጋር በአደባባይ በሚሟገቱበት ጊዜ፤* ብዙ ወንዶች ልጆች ያሉት ሰው በሐሰት ተከሶ ፍርድ ቤት በሚቀርብበት ጊዜ አብረውት የሚቆሙ በርካታ ተሟጋቾች አሉት። ከዚህም በላይ አንድ ሰው በእግዚአብሔር ቸርነት ብዙ ወንዶች ልጆች ካገኘ ይህ ነገር የሚያረጋግጠው በእግዚአብሔር ዘንድ ሞገስ ማግኘቱን ጭምር ነው (128፥3-4 ይመ)። *በአደባ ባይ፤* የከተማ መግቢያ በሮች እንደ ፍርድ አደባባይ ያገለግላሉ (ዘዳ 17፥5፤ 21፥19፤ 22፥15፡24፤ 25፥7፤ ሩት4፥1፤ ኢሳ29፥21 ይመ)።

*መዝ128፤* በእግዚአብሔር መንገድ የሚሄድ የእግዚአብሔር ሰው የተባረከ መሆኑን የሚገልጽ መዝሙር ነው፤ ስለ ቤትና ስለ ንብረት የሚናገር ሌላው የጥበብ ቃል ነው (መዝ127 ይመ)። የመ ዝሙሩ የመዝጊያ ቃል እንደሚያመለክተው መዝሙሩ በመጀመ ሪያ ያገለግል የነበረው ከየቤታቸው መጥተው በኢየሩሳሌም ለማ ምለክ ለተሰበሰቡ ሰዎች የቡራኬ ቃል በመሆን ነበር። የተጻፈ ውም ከምርኮ በፊት ሳይሆን አይቀርም። ባወቃቀር ረገድ ሲታይ በቍ 1-4 ዙሪያ የሚገኘው ቅንብብ ("እግዚአብሔርን የሚፈሩ") እነዚህን ቍጥሮች ከመዝሙሩ ዐቢይ ክፍል/ዋና አካል ይለዩ ታል።

128 *ርእስ፤* የመዝ120 ርእስ ማብ ይመ።

*128፥1-4፤* እግዚአብሔር ሕዝቡን እንደሚባርክ የሚያረጋ ግጥ ክፍል ነው።

128፥1 *የተባረኩ፤* የ1፥1 ማብ ይመ። *እግዚአብሔርን የሚ ፈሩ፤* የ34፥8-14 ማብ ይመ። *በመንገዱም፤* የ25፥4 ማብ ይመ።

*128፥2፤* እግዚአብሔር የድካምን ፍሬ ይባርካል።

*128፥3፤ ታማኝና ፍሬያም ናት። ወይን፤* የፍሬያማነት ምሳሌ ነው (ዘፍ49፥22)፣ ማራኪ (ማሕ7፥8-12)፣ አስደሳች (መሳ 9፥13) መሆንን ይገልጻል። *በቤትህ፤* ይህች ሴት እንደማትታመ ነውና "እግሮቿም በቤቷ አይቀመጡም" (ምሳ7፥11) እንደ ተባለ ችው ሴት አይደለችም። *ወይራ ተክል፤* ምን ጊዜም ለምለም ዛፍ ሲሆን ይህም ረጅም ዘመን እንደሚኖርና ፍሬያማ እንደሚሆን ተስፋ የሚሰጥ ነው። በብሉይ ኪዳን ውስጥ የወይን ተክልና የወ ይራ ዛፍ አብዛኛውን ጊዜ በአንድነት ተጠቅሰዋል (ለምሳሌ በዘፀ 23፥11 ላይ እንደ ተጻፈው ማለት ነው)። እነዚህ ሁለት ተክሎች ብዙ ዘመን መኖር የሚችሉ ከመሆናቸውም በላይ የወይን ጠጅና የወይራ ዘይት ምርት የሚያስገኙ፣ በሕዝቡም የዕለት ተዕለት ኑሮ ውስጥ ከፍ ያለ ሚና የሚጫወቱ ተክሎች ናቸው። *በማእ ድህ ዙሪያ፤* የእያንዳንዱን ቤት ሰብ የዕለት ተለት ምግብ ወደ አንድ ታላቅ ቤተ ሰባዊ ደስታ ይለውጣል።

*128፥5-6፤* የቡራኬ ቃል ሲሆን ይህም እውነተኛ በረከት ምን ምን እንደሚያጠቃልል ይገልጻል፤ እውነተኛ በረከት የማያ ቋርጥ ብልጽግናን፣ ከእግዚአብሔር ጋር የጠበቀ ግንኙነትንና የጸና ሕልውናን (ኢየሩሳሌም የምትበለጽገው ከእግዚአብሔር ጋር የጠበቀ ግንኙነትና የጸና ሕልውና ሲኖራት ነው) እንዲሁም ረጅም ዘመን መኖርን ያጠቃልላል።

128፥5 *ከጽዮን፤* 9-11 እና ማብ፤ እንዲሁም 20፥2፤ 135፥21 ይመ።

128፥6 *በእስራኤል ላይ ሰላም ይውረድ፤* 125፥5 እና ማብ ይመ።

*መዝ129፤* በየጊዜው የሚነሡባት ኀያላን ጠላቶቿ ሁሉ እንደ ቅጠል እንዲረግፉ እስራኤል በየጊዜው የምታቀርበው ጸሎት ነው። እግዚአብሔር ስለታደጋቸው ክብረ በዓል አድር ገዋል (ቍ4)፤ ምናልባት እዚህ ላይ ክብረ በዓል ያደረጉት ከባቢ ሎን ምርኮ ስለታደጋቸው ሊሆን ይችላል። እንደ መዝ128 ሁሉ ይህም መዝሙር የተበጀው በተመጣጠኑ ሁለት አንጓዎች ነው።

129 *ርእስ፤* የመዝ120 ርእስ ማብ ይመ።

*129፥1-4፤* ክፉ ጨቋኞች ብርቱ እንደሆኑ አይኖሩም።

129፥1 *ከልጅነቴ ጀምሮ፤* እስራኤል በግብፅ በባርነት ሥር ከነበረችበት ጊዜ አንሥቶ በኀያላን ጠላቶቿ እጅ ብዙ ግፍና መከራ ደርሶባታል።

129፥2 *ድል አላደረጉኝም፤* እስራኤልን ፈጽመው ሊያጠፏት ወይም ለዘላለም ቀጥቅጠው በባርነት ሊገዟት አል ቻሉም።

129፥4 *ጻድቅ፤* የ4፥1 ማብ ይመ።

የከፋዎችን ገመድ በጣጥሶ ጣለው::

5ጽዮንን የሚጠሉ ሁሉ፣
 ዐፍረው ወደ ኋላቸው ይመለሱ::
6ገና ከመብቀሉ እንደሚደርቅ፣
 በጣራ ላይ እንደ በቀለ ሣር ይሁኑ፤
7ደግሞም ለዐጫጅ እጁን፣
 ለነዶ ሰብሳቢ ዕቅፉን እንደማይሞላ
  ይሁኑ::
8መንገድ ዐላፊዎችም፣
 “*የእግዚአብሔር* በረከት በእናንተ ላይ
  ይሁን፤
 *በእግዚአብሔር* ስም እንባርካችኋለን”
  አይበሉ::

## መዝሙር 130

## ለርዳታ የቀረበ ጥሪ

*መዝሙረ መዐርግ*

1*እግዚአብሔር* ሆይ፤
 ከጥልቅ ወደ አንተ እጮኻለሁ::
2ጌታ ሆይ፤ ድምፄን ስማ፤
 ጆሮዎችህ የልመናዬን ቃል፣
 የሚያዳምጡ ይሁኑ::
3*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ኀጢአትን ብትቈጣጠር፣
 ጌታ ሆይ፤ ማን ሊቆም ይችላል?
4ነገር ግን በአንተ ዘንድ ይቅርታ አለ፤
 ስለዚህም ልትፈራ ይገባሃል::
5*እግዚአብሔርን* ደጅ እጠናለሁ፤ ነፍሴም
 በትዕግሥት ትጠብቀዋለች፤
 በቃሉም ተስፋ አደርጋለሁ::
6ዘብ ዐዳሪ ንጋትን ከሚጠባበቅ ይልቅ፣
 አዎን፤ ዘብ ዐዳሪ ንጋትን ከሚጠባበቅ
  ይልቅ፣
 ነፍሴ ጌታን ትጠባበቃለች::
7*በእግዚአብሔር* ዘንድ ምሕረት፣
 በእርሱም ዘንድ ማዳን አለና፣
 እስራኤል ሆይ፤ *በእግዚአብሔር*
  ተስፋ አድርግ::
8እርሱም እስራኤልን፣
 ከኀጢአቱ ሁሉ ያድነዋል::

## መዝሙር 131

## በእግዚአብሔር መታመን

*የዳዊት መዝሙረ መዓርግ*

1*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ልቤ አልታበየም፤
 ዐይኔ ከፍ ከፍ አላለም፤
ሐሳቤ ለዐጒል ትልቅነት አልተነሣሣም፤
 ከዐቅሜም በላይ አልተንጠራራሁም::
2ነገር ግን ነፍሴን ጸጥ፣ ዝም አሰኘኋት፤
 ጡት የጣለ ልጅ ዐርፎ እናቱ ላይ
  እንደሚቀመጥ፣
 ነፍሴ ጡት እንዳስተዉት ሕፃን በውስጤ
  ጸጥ አለች::
3እስራኤል ሆይ፤ ከአሁን ጀምሮ ለዘላለም፣
 *በእግዚአብሔር* ተስፋ አድርግ::

129፥5 መዝ70፥2፤ ሚክ4፥11
129፥6 2ነገ19፥26፤ መዝ102፥11፤ኢሳ 37፥27
129፥7 ዘዳ28፥38፤ መዝ79፥12
129፥8 መዝ118፥26
130፥1 ኢዮ30፥19፤ መዝ22፥2፤42፥7፤55፥ 17፤142፥5፤ሰቆ3፥55
130፥2 2ዜና6፥40 ፤መዝ27፥7፤28፥2፡6፤ 31፥22፤86፥6፤140፥6
130፥3 1ሳሙ6፥20 ፤ዕዝ9፥15፤መዝ143፥2 ፤ናሆ1፥6፤ራእ6፥17
130፥4 ዘፀ34፥7፤ 2ሳሙ24፥14፤1ነገ 8፥40፤ኤር31፥34
130፥5 መዝ5፥3፤ 27፥14፤119፥74፤ኢሳ 8፥17፤26፥8፤30፥18፤ 49፥23
130፥6 2ሳሙ23፥4 ፤መዝ63፥6
130፥7 1ዜና21፥13 ፤መዝ25፥5፤71፥14፤ 111፥9፤ሮሜ3፥24
130፥8 ዘፀ34፥7፤ ሉቃ1፥68፤ማቴ1፥21
131፥1 2ሳሙ22፥ 28፤ኢዮ5፥9፤41፥34፤ መዝ101፥5፤139፥6፤ ኢሳ2፥12፤ኤር45፥5፤ ሮሜ12፥16
131፥2 መዝ116፥7 ፤ማቴ18፥3፤1ቆሮ 13፥11፤14፥20
131፥3 መዝ25፥5፤113፥2፤119፥43፤130፥7

*129፥5-8፤* ጽዮንን የሚጠሉ ሁሉ እንደ ደረቀ ዛፍ ይሁኑ::

*129፥5፤* የ5፥10 ማብ ይመ::

129፥6 *በጣራ ላይ እንደ በቀለ ሣር ይሁኑ፤* የእስራኤልን ጀርባ በጅራፍ የሚተለትሉ (ቍ3)፣ ደረቱን ለፀሓይ በሰጠ ጣራ ላይ በቅሉ እንደደረቀ ሣር ይሁኑ፤ ማንም ዐርሶና አለስልሶ የሚዘራባቸውና ነዶ የሚሰበስብባቸው አይሁኑ (ቍ7)::

129፥8 *የሚያልፉ የሚያገድሙትም፤* በአጫጆቹ እርሻ ላይ የሚያልፉ የሚያገድሙ ሁሉ ከአጫጆች ጋር የደስታ ሰላምታ አይለዋወጡም (ሩት2፥4)፤ ምክንያቱም የአጫጆቹ እጅ ሥራ ይፈታል::

*መዝ130፤* ምንም እንኳ ኀጢአተኛ ቢሆንም ከጥልቅ ሆኖ የሚያሰማውን ጩኸት እግዚአብሔር እንደሚሰማው እርግጠኛ የሆነ ሰው ያቀረበው ምስክርነት ነው:: የመዝሙሩ ቃላት እንደሚያመለክቱት መዝሙሩ የተጻፈው ከምርኮ በኋላ ነው:: መዝሙሩ ከሰባቱ የንስሓ መዝሙሮች (የመዝ6 መግቢያ ይመ) ውስጥ ስድስተኛው ነው:: መዝሙሩ በአራት ቤት የተዋቀረ ሲሆን፣ እያንዳንዳቸው ሁለት ቤት ባላቸው ሁለት ክፍሎች ይከፈላል::

*130ርእስ፤* የመዝ120 ርእስ ማብ ይመ::

*130፥1-4፤* ምሕረትን ለማግኘት የቀረበ ጸሎት ነው፤ ምሕረትን እንደሚያገኝም እርግጠኛ ነው::

130፥1 *ከጥልቅ፤* 69፥2 ላይ እንደ ተጠቀሰው ነው (የ30፥1፤ 32፥6 ማብ ይመ)::

130፥4 *ይቅርታ ... አለ፤* ይህን የተናገረው በዘፀ34፥6-7 ላይ ያሉትን ቃላት እያሰበ ስለ መሆኑ ምንም አያጠራጥርም:: *ትፈራለህ፤* እውነተኛ አምላክ ተደርገህ ትከበራለህ፣ ትመለካለህ፣ ትታመናለህ፣ ትገለገላለህ ማለት ነው:: እግዚአብሔር ይቅር ባይ አምላክ ባይሆን ኖሮ ሰዎች በፍርሀት ተይዘው ከእርሱ ይሸሹ ነበር::

*130፥5-8፤* በእግዚአብሔር የሚታመን መሆኑን የገለጸበት ክፍል ነው፤ የግል ምስክርነቱን በሰፋት ሰጥቶአል (131፥3 ይመ)::

130፥5 *ደጅ እጠናለሁ፤* በተስፋ እጠባበቃለሁ ማለቱ ነው:: *ነፍሴ፤* የ6፥3 ማብ ይመ:: *ቃሉ፤* በተለይም በቃል ኪዳኑ ላይ የተጠቀሱትን የተስፋ ቃሎች ማለት ነው (119፥25:28:37:42: 49:65:74:81:107:114:147 ይመ)::

130፥6 *ዘብ፤* 127፥1፤ 2ሳሙ13፥34፤ 18፥24-27፤ ማሕ3፥3፤ 5፥7 ይመ:: *ንጋት፤* የመዝ57 መግቢያ ይመ፤ የ59፥9 ማብ ይመ::

130፥7 *ምሕረት፤* የ6፥4 ማብ ይመ::

130፥8 *ከኀጢአቱ ሁሉ፤* ኀጢአት ከሚያስከትለው መዘዝ ሁሉ ማለት ነው:: ይህ ታላቅ ተስፋ በክርስቶስ ኢየሱስ ተፈጽሞአል::

*መዝ131፤* በትሕትና በእግዚአብሔር ላይ የሚታመን ሰው የተናገረው ቃል ነው፤ ከመዝ130 ቀጥሉ በመቀመጡ አግባብነት አለው::

131ርእስ *የዳዊት የምዕራግ፤* የመዝ120 ርእስ ማብ ይመ::

131፥1 *ልቤ፤* የ4፥7 ማብ ይመ:: *አልታበየም ... ከፍ ከፍ አላለም፤* ከምንም ነገር ይልቅ ሰውን ከእግዚአብሔር ጋር የሚያጣላው ትዕቢት ነው (የ31፥23 ማብ ይመ፤ ከ2ሳሙ6፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ):: *ለትልቅነት አልተነሣሣም፤* በመካከላቸው አልገኝም፤ አልኖርም፤ ከእነር ሱም ጋር አልተባበርም ማለት ነው:: *ከዐቅሜም በላይ፤* የእግዚአብሔርን ሥራ ከንቱ ለማስቀረት የተፈጸሙ ተግባራት ናቸው:: እዚህ ላይ የተባለው ነገር የሚያተኩረው የእግዚአብሔርን ዐይነት ኀይል ማግኘት ላይ ሳይሆን የእግዚአብሔርን ዐይነት ማስተዋል ማግኘት ላይ ነው::

131፥2 *ነፍሴ፤* የ6፥3 ማብ ይመ:: *ጡት የጣለ ልጅ፤* ከእናቱ አጠገብ እንደማይለይ የአራት ወይም የአምስት ዓመት ሕፃን ማለት ነው::

*131፥3፤* እንደ መዝሙረኛው ሁሉ የእስራኤልም ሕዝብ እግዚአብሔርን ዘወትር ተስፋ አድርጎ መኖር አለበት::

*መዝ132፤* የመዝሙሩ አወቃቀር እንደሚያሳየው በዳዊት ዙፋን ላይ ተቀምጦ ለሚገዛው የዳዊት ልጅ እግዚአብሔር ሞገስ እንዲሆንለት የቀረበ ጸሎት ነው (የቍ10 ማብ ይመ):: የመዝሙሩ ቋንቋ እንደሚያመለክተው መዝሙሩ የተጻፈው በነገሥታት ዘመን ዋዜማ ላይ ነው:: ይህ መዝሙር የተጻፈው በቤተ መቅደሱ ምረቃ በዓል ላይ እንዲዘመር ነው የሚለው አባባል ትክክል ሊሆን ይችላል (ከቍ8-10 ያለውን ከ2ዜና 6፥41-42 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ሆኖም በሥርዐተ ንግሥ ላይ እንዲዘመር ታስቦ የተደረሰ መዝሙር ነው የሚለው አባባልም ሊካድ አይችልም (ከመዝ 2፤72፤110 ጋር ያነጻጽሩ):: የዜና መጻሕፍት ደራሲ ይህን ጸሎት የጸለየው ራሱ ንጉሡ እንደሆነ አድርጎ አቅርቦታል:: መዝሙሩ ሁለት አቤቱታዎች ያሉት ሲሆን (ቍ1:10) ከሁለቱም አቤቱታዎች ቀጥሎ ሁለት ባለ አራት መስመር እንጓዎች

ነው፤ አንዱ እንደሚሞት፣ ሌላውም እንዲሁ ይሞታል። ሁሉ አንድ ዐይነት እስትንፋስ[a] አላቸው፤ ሰውም ከእንስሳ ብልጫ የለውም፤ ሁሉም ከንቱ ነው። [20]ሁሉም ወደ አንድ ቦታ ይሄዳሉ፤ ሁሉም ከዐፈር እንደ ሆኑ፣ ተመልሰው ወደ ዐፈር ይሄዳሉ። [21]"የሰው መንፈስ ወደ ላይ መውጣቱን፣ የእንስሳ እስትንፋስ[b] ደግሞ ወደ ታች ወደ ምድር መውረዱን ማን ያውቃል?"

[22]ስለዚህ ለሰው ዕጣ ፈንታው ስለ ሆነ፣ በሥራው ከመደሰት የተሻለ ነገር እንደ ሌለው አየሁ፤ ከእርሱ በኋላ የሚሆነውንስ ተመልሶ እንዲያይ የሚያደርገው ማን ነው?

## ግፍ፣ ጥረት፣ ብቸኝነት

**4** እንደ ገና ከፀሓይ በታች የሚደረገውን ግፍ ሁሉ አየሁ፤ አስተዋልሁም፤

የተገፉትን ሰዎች እንባ ተመለከትሁ፤
የሚያጽናናቸውም አልነበረም፤
ኀይል በሚገፏቸው ሰዎች እጅ ነበረ፤
የሚያጽናናቸውም አልነበረም።
[2]እኔም የቀድሞ ሙታን፣
ዛሬ በሕይወት ካሉት ሕያዋን ይልቅ፣
ደስተኞች እንደ ሆኑ ተናገርሁ።
[3]ነገር ግን ከሁለቱም ይልቅ፣
ገና ያልተወለደው፣
ከፀሓይ በታች የሚደረገውንም፣
ክፋት ያላየው ይሻላል።

[4]እንዲሁም ጥረትና የሥራ መከናወን ሁሉ ሰው በባልንጀራው ላይ ካለው ቅናት እንደ ሚመነጭ ተመለከትሁ፤ ይህም ደግሞ ከንቱ፣ ነፋስንም እንደ መከተል ነው።

[5]ሰነፍ እጁን አጣጥፎ ይቀመጣል፤
የገዛ ራሱንም ሥጋ ይበላል።
[6]በድካምና ነፋስን በመከተል
ከሚገኝ ሁለት ዕፍኝ ይልቅ፣
በርጋታ የሚገኝ አንድ ዕፍኝ ይሻላል።

[7]ደግሞም ከፀሓይ በታች ከንቱ የሆነን ነገር አየሁ፤

[8]ልጅም ሆነ ወንድም የሌለው፣
ብቸኛ ሰው አለ፤
ጥረቱ ማለቂያ የለውም፤
ዐይኑም ባለው ሀብት ገና አልረካም፤
እርሱም፣ "ለማን ብዬ ነው የምደክመው?
ራሴን ከማስደሰትስ የምቈጠበው
ለምንድን ነው?" ብሎ ጠየቀ፤
ይህም ደግሞ ከንቱ፣
የጭንቅ ኑሮ ነው።
[9]ለሥራቸው መልካም ውጤት ስለሚያገኙ፣
ከአንድ፣ ሁለት መሆን ይሻላል፤
[10]አንዱ ቢወድቅ፣
ባልንጀራው ደግፎ ያነሣዋል።
ቢወድቅ የሚያነሣው ረዳት የሌለው ግን፣
እንዴት አሳዛኝ ነው!
[11]ደግሞም ሁለቱ አብረው ቢተኙ
ይሞቃቸዋል፤
ነገር ግን አንዱ ብቻውን እንዴት
ሊሞቀው ይችላል?
[12]አንድ ሰው ብቸኛውን ቢያጠቃውም፣
ሁለት ከሆኑ ይመክቱታል፤
በሦስት የተገመደ ገመድም ቶሎ
አይበጠስም።

## በልጦ መገኘት ከንቱ ነው

[13]ምክርን መቀበል ከማያውቅ ሞኝና ሽማግሌ ንጉሥ ይልቅ ጠቢብ የሆነ ድኻ ወጣት ይሻላል። [14]ወጣቱ ከእስር ቤት ወደ ንጉሥነት የመጣ ወይም በግዛቱ ውስጥ በድኽነት የተወለደ ሊሆን ይችላል። [15]ከፀሓይ በታች የሚኖሩና የሚመላለሱ ሁሉ፣ ንጉሡን የሚተካውን ወጣት ተከትለውት አየሁ። [16]በፊቱ የነበረው ሕዝብ ሁሉ ቍጥር ስፍር አልነበረውም፤ ከእርሱ በኋላ የመጡት ግን በተተኪው አልተደሰቱም። ይህም ደግሞ ከንቱ፣ ነፋስንም እንደ መከተል ነው።

[a]19 ወይም መንፈስ
[b]21 ወይም የሰው መንፈስ ወደ ላይ እንደሚሄድ ወይም የእንስሳት መንፈስ

3፥19 መክ2፥14
3፥20 ዘፍ2፥7፤ ኢዮ34፥15
3፥21 መክ12፥7
3፥22 ኢዮ31፥2፤ መክ2፥24
4፥1 መዝ12፥5፤ ሰቆ1፥16
4፥2 ኢዮ3፥17፤ 10፥18፤ኤር20፥17-18፤22፥10
4፥3 ኢዮ3፥16:22
4፥4 መክ1፥14
4፥5 ምሳ6፥10
4፥6 ምሳ15፥16-17፤ 16፥8
4፥8 ምሳ27፥20

3፥19 *አንድ ዐይነት እስትንፋስ፤* መዝ 104፥27-30 ይመ።

3፥20 *ወደ አንድ ቦታ፤* ወደ ገነት ወይም ወደ ሲኦል ሳይሆን፣ በግልጽ እንደሚታየው፣ እንስሳት ወደ ዐፈር እንደሚመለሱ ሁሉ፣ የሰውም ዕጣ ፈንታ ወደ ዐፈር መመለስ እንደ ሆነ ያመለክታል፤ ሕይወት ያላቸው ነገሮች ሁሉ በሞት እኩል ናቸውና (ዘፍ 3፥19፤ መዝ103፥14 ይመ)።

3፥21 *ማን ያውቃል?* 2፥19 እና ማብ ይመ፤ ከ12፥7 ጋር ያነጻጽሩ። ከመገመት በስተቀር ሰው በራሱ ትክክለኛውን ነገር ሊያውቅ አይችልም። ለጥያቄው የተሰጠው መልስ በመጀመሪያ ግልጽ አልነበረም (መዝ16፥9-11፤ 49፥15፤ 73፥23-26፤ ኢሳ 26፥19፤ ዳን12፥2-3)፤ በኋላ ግን በወንጌል አማካይነት ግልጽ ሆኖአል (2ጢሞ1፥10)።

3፥22 *የተሻለ ነገር እንደሌለው፤ ሥራውም* ቢሆን በራሱ የመጨረሻ ተደርጎ ከተወሰደ ትርጕም አይሰጥም (4፥4፤ 9፥9 ይመ)። ሥራን ከእግዚአብሔር የተሰጠ ጸጋ አድርገው ከተቀበሉት (ቍ 13) ግን ዋጋ አለው (ቍ 14)።

4፥1 *ግፍ፤* በ3፥16 ላይ የተጠቀሰ መሪ ሐሳብ ሲሆን፣ በሰው ሕይወት ውስጥ ከሚከሠቱ አሳዛኝ ነገሮች አንዱ ነው። ሕይወት ትርጕም ሲያጣ ያሳዝናል። በሕይወት አስከፊ ገጽታ ውስጥ ማለፍ ደግሞ እጅግ ይመራል።

4፥2 *ካሉት ሕያዋን ይልቅ ደስተኞች፤* ኢዮ3፤ ኤር 20፥14-18 ይመ። የበለጠውን ነገር ተስፋ ስለሚያደርግ እምነት ለማስተዋል ሮሜ 8፥35-39 ይመ።

*4፥4-6፤ ሥራ መሥራትም* ሆነ አለመሥራት ደስታ አያስገኝም።

4፥4 *ጥረትና የሥራ መከናወን ሁሉ፤* እግዚአብሔር ካልባረከው፣ ይህም ቢሆን ከንቱ ነው (3፥13 ይመ፤ ዘፍ39 ላይ ካለው የዮሴፍ ታሪክ ጋር ያነጻጽሩ)።

*4፥5፤* በ10፥18፤ ምሳ 6፥6-11፤ 24፥30-34 ላይ የሰነፍ ሰው ውድቀት ምን እንደሚመስል በግልጽ ተጠቅሶአል።

4፥6 *በርጋታ፤* ምሳ 30፥7-9 ይመ። ጳውሎስ በዚህ ሐሳብ ላይ የመጨረሻውን ቃል ይናገራል (ፊል 4፥11-13)።

*4፥7-12፤* ክርስቲያን ያልሆነ ብቸኛ ሰውም ቢሆን፣ ሕይወቱ ትርጕም የለሽና አስቸጋሪ ይሆንበታል።

4፥12 *ሁለት ... በሦስት፤* ከፍተኛ ጥንካሬን የሚያሳይ አገላለጽ ነው።

*4፥13-16፤* ያለ እግዚአብሔር ፈቃድ የሚደረግ ሩጫ የዓለማውያን ሕይወት ትርጕም የለሽነት ሌላው ምሳሌ ነው።

*5፥1-7፤* የዚህ ክፍል መሪ ሐሳብ ጥራዝ ነጠቅ ሃይማኖት ከንቱ መሆኑን የሚያመለክት ነው፤ ይህም በችኰላ ስእለት መሳል

## እግዚአብሔርን ፍራ

5 ወደ እግዚአብሔር ቤት ስትሄድ እግርህን ጠብቅ:: ለመስማት መቅረብ የሰነፎችን መሥዋዕት ከማቅረብ ይበልጣል፤ እነርሱ ክፉ እንደሚሠሩ አያውቁምና::

2በአፍህ አትፍጠን፤
በእግዚአብሔርም ፊት ማንኛውንም ነገር
ለመናገር፣
በልብህ አትቸኵል፤
እግዚአብሔር በሰማይ፣
አንተ ደግሞ በምድር ነህ፤
ስለዚህ ቃልህ ጥቂት ይሁን::
3በሥራ ብዛት ሕልም እንደሚታይ፣
ብዙ ቃል ባለበትም የሞኝ ንግግር
ይገለጣል::

4ለእግዚአብሔር ስእለትን በተሳልህ ጊዜ ለመፈጸም አትዘግይ፤ በሰነፎች ደስ አይለውምና፤ ስእለትህን ፈጽም:: 5ስእለት ተስሎ ካለመፈጸም፣ አለመሳል ይሻላል:: 6አንደበትህ ወደ ኀጢአት እንዲመራህ አትፍቀድ፤ ለቤተ መቅደስ መልእክተኛም፣ "የተሳልሁት በስሕተት ነበር" አትበል:: እግዚአብሔር በተናገርኸው ተቈጥቶ የእጅህን ሥራ ለምን ያጥፋ? 7ብዙ ሕልምና ብዙ ቃል ከንቱ ነው፤ ስለዚህ እግዚአብሔርን ፍራ::

## ባለጠግነት ከንቱ ነው

8በአገር ውስጥ ድኻ ተጨቍኖ፣ ፍትሕ ተጓድሎ፣ መብትም ተረግጦ ብታይ፣ እንደ ነዚህ ባሉ ነገሮች አትደነቅ፤ ምክንያቱም አንዱን አለቃ የበላዩ ይመለከተዋል፤ በእነዚህ በሁለቱም ላይ ሌሎች ከፍ ያሉ አሉ:: 9ከምድሩ የሚገኘው ትርፍ ለሁሉም ነው፤ ንጉሡም ራሱ የሚጠቀመው ከዕርሻ ነው::

10ገንዘብን የሚወድ፣ ገንዘብ አይበቃውም፤
ብልጽግናንም የሚወድ፣ በትርፉ አይረካም፤
ይህም ከንቱ ነው::
11ሀብት በበዛ ቍጥር፣
ተጠቃሚውም ይበዛል፤
በዐይኑ ብቻ ከማየት በቀር
ታዲያ፣ ለባለቤቱ ምን ይጠቅመዋል?
12ጥቂትም ይሁን ብዙ ቢበላ፣
የሠራተኛ እንቅልፍ ጣፋጭ ነው፤
የሀብታም ሰው ብልጽግና ግን
እንቅልፍ ይነሣዋል::
13ከፀሓይ በታች የሚያሳዝን ክፉ ነገር አየሁ፦
ይህም ለባለቤቱ ጕዳት የተከማቸ ሀብት፣
14ወይም በአንድ መጥፎ አጋጣሚ የጠፋ
ብልጽግና ነው፤
ልጅ ሲወልድም፣
ለእርሱ የሚያስቀርለት ምንም ነገር
አይኖርም::
15ሰው ከእናቱ ማሕፀን
ዕራቍቱን ይወለዳል፤
እንደ መጣው እንዲሁ ይመለሳል::
ከለፋበትም ነገር፣
አንድም እንኳ በእጁ ይዞ ሊሄድ አይችልም::
16ይህ ደግሞ እጅግ ክፉ ነገር ነው፤
ሰው እንደ መጣ እንዲሁ ይሄዳል፤
የሚደክመው ለነፋስ ስለ ሆነ፣
ትርፉ ምንድ ነው?
17በብዙ ጭንቀት፣ መከራና ብስጭት፣
ዘመኑን ሁሉ በጨለማ ውስጥ ይበላል::

18የሰው ዕጣው ይህ ስለ ሆነ፣ እግዚአብሔር በሰጠው በጥቂት ዘመኑ ከፀሓይ በታች በሚደክምበት ነገር ርካታን ያገኝ ዘንድ፣ መብላቱና መጠጣቱም መልካምና ተገቢ መሆኑን ተገነዘብሁ:: 19እግዚአብሔር ለሰው ባለጠግነትና ሀብት መስጠቱ፣ እንዲደሰትበትም ማስቻሉ፣ ዕጣውን እንዲቀበልና በሥራውም እንዲደሰት ማድረጉ፣ ይህ የእግዚአብሔር ስጦታ ነው:: 20እግዚአብሔር የልብ ደስታ ስለሚሰጠውም በሕይወቱ ዘመን ያሉትን ቀናት እምብዛም አያስባቸውም::

6 ከፀሓይ በታች ሌላ ክፉ ነገር አየሁ፤ እርሱም ለሰዎች እጅግ የሚከብድ ነው፤ 2ሰው ልቡ የሚሻውን እንዳያጣ፣ እግዚአብሔር ባለጠግነትን፣ ሀብትንና ክብርን ይሰጠዋል፤ እግዚአብሔር ግን እንዲደሰትበት ሥልጣን አልሰጠውም፤ ይልቁን ባዕድ ይደሰትበታል:: ይህም ከንቱ፣ እጅግም ክፉ ነገር ነው::

5፥2 መሳ11፥35፤ ኢዮ6፥24፤ ምሳ20፥25
5፥3 ኢዮ20፥8፤ መክ10፥14
5፥4 ዘኍ30፥2-4፤ ዘዳ23፥21፤መሳ 11፥35፤መዝ66፥13-14፤119፥60
5፥5 ዘኍ30፥24፤ ዮና2፥9
5፥7 መክ3፥14
5፥8 መዝ12፥5
5፥12 ኢዮ20፥20
5፥13 መክ6፥1-2
5፥15 ኢዮ1፥21፤ መዝ49፥17፤ መክ1፥3፤1ጢሞ6፥7
5፥16 መክ1፥3
5፥18 መክ2፥3፡24
5፥19 1ዜና29፥12፤ ኢዮ31፥2፤ መክ2፥24፤6፥2
5፥20 ዘዳ12፥7፡18
6፥2 መክ5፥13፡19

በሚያስከትለው መዘዝ ተንጸባርቆአል::

5፥1 *እግርህን ጠብቅ፤* ምን ማለትና ምን ማድረግ እንደሚገባህ በጥንቃቄ አስብ ማለት ነው:: *ለመስማት፤* መታዘዝን ያመለክታል:: በ1ሳሙ 15፥22 ላይም ጸሓፊው የዚህን ቃል የዕብራይስጥ ግስ በመጠቀም እውነተኛውን አምልኮ እውነተኛ ካልሆነው አምልኮ ጋር ያነጻ ጽራል:: *መሥዋዕት፤* ምናልባት በቍ 4-6 ላይ ከተጠቀሰው ስእለት ጋር የተያያዘ ይሆናል::

5፥2 *በአፍህ አትፍጠን፤* ፈጥኖ ስእለትን እንደ መሳል ያለውን ነገር ማድረግ ትክክል እንዳልሆነ ያሳያል::

*5፥3፤* ምሳሌያዊ አነጋገር ነው:: የተራበ ሰው ድግስ ባጋጠመኝ ብሎ እንደሚያስብ፣ የተጨነቀም ሰው ታላቅ ደስታን ይመኛል፤ በምኞቱም ውስጥ ሆኖ ብዙ ቃል በመናገር በችኰላ ለእግዚአብሔር ስእለት ይሳላል (ቍ 7 ይመ)::

5፥4 *ስእለትን፤* ዘዳ 23፥21-23፤ 1ሳሙ1፥11፡24-28 ይመ:: *በሰነፎች ደስ አይለውምና፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ሰነፍ መማር የማይችል ብቻ ሳይሆን፣ የማይፈልግም መሆኑ ተገልጾአል (ምሳ 1፥20-27፤ የዕብራይስጡ ቃል የሥነ ምግባር ጕድለት መሆኑን ያመለክታል)::

5፥6 *መልእክተኛም፤* ሚል 2፥7 ይመ::

5፥8 *አትደነቅ፤* ስለ ኅብረተ ሰብ የሚናገረውን ሌላ ክፍል ለማስተዋል 4፥1-3 ይመ:: በሰው ልብ ያለውን እንደሚያቀው እንደ ኢየሱስ (ዮሐ 2፥25)፣ ይህ ሰባኪ የተሳሳተ ወይም ተምኔታዊ ሐሳብ አልነበረውም::

5፥9 *ንጉሡም ... የሚጠቀመው ከእርሻ ነው፤* የአሞ 7፥1 ማብ ይመ::

*5፥10፤* የሀብት ብዛት ርካታን አያስገኝም (1ጢሞ 6፥9-10 ይመ)::

*5፥11-12፤* ሀብት ሲበዛ ጭንቀትን ያስከትላል::

5፥13 *ጕዳት፤* የሀብት ብዛት ከሚያመጣው ሥጋት የተነሣ ማለት ነው::

5፥15 *አንድም እንኳ ... ይዞ፤* ሉቃ 12፥14-21 ይመ::

*5፥18-20፤* የ2፥24-25 ማብ ይመ::

6፥2-3፡6 *እንዲደሰትበት፤* በቍ 2 ላይ የተጠቀሰው ሐሳብ ከ5፥19 ጋር ሲነጻጸር፣ እግዚአብሔር በሰጠው በረከት በመጠቀም የሚገኘው ደስታ የእግዚአብሔር ነጻ ስጦታ እንጂ መብት እንዳልሆነ ያመለክታል:: እግዚአብሔር ይህን እውነት የሚዘነጋውን

[3]አንድ ሰው መቶ ልጅ ሊኖረውና ብዙ ዓመት ሊኖር ይችላል፤ ምንም ያህል ይኑር፣ በሀብቱ ደስ ካልተሰኘበትና በአግባብ ካልተቀ በረ፣ ከእርሱ ይልቅ ጭንጋፍ ይሻላል እላ ለሁ፤ [4]ምክንያቱም በከንቱ ይመጣል፤ በጨ ለማም ይሄዳል፤ ስሙም በጨለማ ተሸፍኖ አል። [5]ፀሓይን ባያይና ምንም ነገር ባያውቅ እንኳ፣ እርሱ ከዚያ ሰው ይልቅ ዕረፍት አለው፤ [6]ሁለት ጊዜ ሺህ ዓመት ቢኖር ነገር ግን በሀብቱ ደስ ባይሰኝበት ሁሉ ወደዚያ ስፍራ የሚሄድ አይደለምን?

[7]የሰው ጥረት ሁሉ ለአፉ ነው፤
ፍላጎቱ ግን ፈጽሞ አይረካም።
[8]ጠቢብ ከሞኝ ይልቅ ምን ብልጫ አለው?
ድኻስ በሌሎች ፊት እንዴት እንደሚኖር
በማወቁ፣
ትርፉ ምንድን ነው?
[9]በምኞት ከመቅበዝበዝ፣
በዐይን ማየት ይሻላል፤
ይህም ደግሞ ከንቱ፣
ነፋስንም እንደ መከተል ነው።

[10]አሁን ያለው ሁሉ አስቀድሞ ስም
የተሰጠው ነው፤
ሰው የሚሆነውም አስቀድሞ የታወቀ
ነው፤
ከራሱ ይልቅ ከሚበረታ ጋር፣
ማንም አይታገልም።
[11]ቃል በበዛ ቍጥር፤
ከንቱነት ይበዛል፤
ይህ ታዲያ ለሰው ምን ይጠቅማል?

[12]ሰው በሕይወት ሳለ፣ እንደ ጥላ በሚያ ልፉት ጥቂትና ከንቱ በሆኑት ቀኖቹ፣ ለሰው መልካም የሆነውን የሚያውቅ ማን ነው? እርሱ ከሄደ በኋላስ ከፀሓይ በታች የሚሆነ ውን ማን ሊነግረው ይችላል?

## ጥበብ

**7** መልካም ስም ከመልካም ሽቱ ይበልጣል፤
ከልደትም ቀን የሞት ቀን ይሻላል።
[2]ወደ ግብዣ ቤት ከመሄድ፣
ወደ ሐዘን ቤት መሄድ ይሻላል፤
ሞት የሰው ሁሉ ፍጻሜ ነውና፤
ሕያው የሆነም ይህን ልብ ማለት
ይገባዋል።
[3]ሐዘን ከሣቅ ይሻላል፤
ያዘነ ፊት ለልብ መልካም ነውና።
[4]የጠቢባን ልብ በሐዘን ቤት ነው፤
የሞኞች ልብ ግን በደስታ ቤት ነው።
[5]የሞኞችን መዝሙር ከመስማት፣
የጠቢባንን ሰዎች ተግሣጽ መስማት
ይሻላል።
[6]የሰነፎች ሣቅ፣
ከድስት ሥር እንደሚንጣጣ የእሾኽ ማገዶ
ነው፤
ይህም ደግሞ ከንቱ ነው።

[7]ግፍ ጠቢብን ሞኝ ያደርጋል፤
ጒቦም ልብን ያበላሻል።

[8]የአንድ ነገር ፍጻሜ ከጅማሬው ይሻላል፤
ትዕግሥተኛም ከትዕቢተኛ ይሻላል፤
[9]የሞኞች ቍጣ በዕቅፋቸው ውስጥ ስለ ሆነ፣
በመንፈስህ ለቍጣ አትቸኵል።

[10]አንተም፣ "ከእነዚህ ቀናት የቀድሞዎቹ ለምን
ተሻሉ?" አትበል፤
እንዲህ ያሉትን ጥያቄዎች መጠየቅ
ጠቢብነት አይደለምና።

[11]ጥበብ እንደ ርስት መልካም ነገር ነው፤
ጠቃሚነቱም ፀሓይን ለሚያዩ ሰዎች
ነው።
[12]ገንዘብ ጥላ ከለላ እንደ ሆነ ሁሉ፣
ጥበብም ጥላ ከለላ ነው፤
የዕውቀት ብልጫዋ ግን፣
ጥበብ የባለቤቷን ሕይወት መጠበቋ
ነው።

[13]እግዚአብሔር ያደረገውን ተመልከት፤

እርሱ ያጣመመውን፣
ማን ሊያቃናው ይችላል?
[14]ጊዜው መልካም ሲሆን፣ ደስ ይበልህ፤
ጊዜው ክፉ ሲሆን ግን ይህን አስብ፤
እግዚአብሔር አንዱን እንዳደረገ፣
ሌላውንም አድርጎአል፤
ስለዚህ ሰው ስለ ወደ ፊት ሁኔታው፣

6፥3 ኢዮ 3፥3፡6
6፥6 መክ2፥14
6፥7 ምሳ27፥20
6፥8 መክ2፥15
6፥9 መክ1፥14
6፥10 መክ3፥15
6፥12 1ዜና29፥15፤ ኢዮ10፥20፤14፥2፤ 20፥8፤መዝ39፥6
7፥1 ኢዮ10፥18፤ ምሳ22፥1፤ማሕ1፥3
7፥2 ምሳ11፥19፤ መክ2፥14
7፥3 ምሳ 14፥13
7፥4 መክ2፥1፤ ኤር16፥8
7፥5 ምሳ13፥18፤ 15፥31-32
7፥6 መዝ58፥9፤ ምሳ14፥13
7፥7 ዘፀ18፥21፤ 23፥8
7፥8 ምሳ14፥29
7፥9 ምሳ14፥29፤ ማቴ5፥22
7፥10 መዝ77፥5
7፥11 መክ2፥13፤ 11፥7
7፥13 መክ1፥5፤ 2፥24
7፥14 ኢዮ1፥21፤ መክ2፥24

ሰው ሞኝ ይለዋል (ሉቃ 12፥20)።

6፥3 *በሚገባ ካልተቀበረ፤* እንደ ንጉሥ ኢዮአቄም (ኤር 22፥18-19) ሳይለቀስለትና ተገቢው ክብር ሳይሰጠው እንደ ሚቀበር ያመለክታል። *ጭንጋፍ፤* ለዓለማዊ ሰው፣ ሕይወት ወደ ሞት የሚወስድ ከንቱ ጒዞ ነው፤ አቋራጩና ቀላሉ መንገድ ሞቶ መወለድ ነው (ከኢዮ 3፥16፤ ከመዝ 58፥8 ጋር ያነጻጽሩ)።

6፥6 *ወደዚያ ስፍራ፤* እዚህም ላይ ከሞት በኋላ ስለሚሆ ነው ሳይሆን (ቍ12፤ 2-21 ይመ)፣ ሰው ሁሉ ሟች ስለ መሆኑ ይገልጻል።

*6፥7-12፤* ሰባኪው በራስ መርካትን በመቃወም የተለያዩ ሐሳ ቦችን ይጠቍማል፤ የሕይወት ጥቅም ጊዜያዊ (ቍ 7)፣ አወዛጋቢ (ቍ8) እና የማይጨበጥ መሆኑን (ቍ9)፣ የፈጠራ ችሎታችን፣ ኀይላችንና ጥበባችንም ውሱን መሆኑን (ቍ10-11)፣ እንዲሁም ከሰው የሚገኝ ጥቅምና ወደፊት ሊሆን ያለው ነገር አስተማማኝ አለመሆኑን (ቍ12) ይናገራል።

6፥10 *ስም የተሰጠው፤* አስቀድሞ በእግዚአብሔር የተወሰነ መሆኑን ያሳያል። *የታወቀ፤*አስቀድሞ በእግዚአብሔር መታወቁን ያመለክታል። *ከራሱ ይልቅ ከሚበረታ፤* እግዚአብሔርን የሚያመለክት ነው።

6፥12 *እንደ ጥላ፤* 1ዜና 29፥15 ይመ።

7፥1 *የሞት ቀን፤* ለክርስቲያን ከሚወለድበት ቀን ይልቅ የሚሞትበት ቀን ይሻለዋል፤ ከእግዚአብሔር ጋር ለዘላለም ለመ ኖር እጅግ የተሻለውን አዲስ ሕይወት የሚጀምርበት ዕለት ነውና (2ቆሮ 5፥1-10፤ ፊል 1፥21-23)። ከደስታ ጊዜ ይልቅ በችግር ጊዜ ብዙ ነገር ልንማር እንደምንችል ሰባኪው በቍ 2-6 ላይ ገልጾአል።

7፥7 *ጒቦም፤* ማቴ28፥11-15፤ ሉቃ22፥4-6 ይመ።

7፥9 *ቍጣ፤* ምሳ16፥32፤ 17፥14፤ 1ቆሮ13፥4-5 ይመ።

7፥12 *ሕይወት መጠበቋ፤* ለዚህ ሐረግ የተሰጠው የዕብራ ይስጥ አገላለጽ፣ "ሕይወት ይሰጣል" ወይም "ሕይወት ያድሳል" ማለት ሊሆን ይችላል (ምሳ 3፥13-18፤ 13፥14 ይመ)።

7፥13 *ማን ሊያቃናው ይችላል?* የእግዚአብሔርን ማንነት ያሳስባል፤ እግዚአብሔር የወሰነውን ነገር ሰው ሊለውጠው አይች ልም (የ1፥15 ማብ ይመ)።

7፥14 *እግዚአብሔር አንዱን እንዳደረገ፣ ሌላውንም አድ ርጎአታል፤* ከሮሜ 8፥28-29 ጋር ያነጻጽሩ።

ምንም ሊያውቅ አይችልም።

[15]በዚህ ከንቱ በሆነው ሕይወቴ እነዚህን ሁለቱን ነገሮች አይቻለሁ፤

ጻድቅ በጽድቁ ሲጠፋ፣
ኀጥእም በክፋቱ ዕድሜው ሲረዝም።
[16]እጅግ ጻድቅ፣
እጅግም ጠቢብ አትሁን፤
ራስህን ለምን ታጠፋለህ?
[17]እጅግ ክፉ አትሁን፤
ሞኝም አትሁን፤
ለምንስ ያለ ቀንህ ትሞታለህ?
[18]አንዱን ይዞ ሌላውንም አለመልቀቅ
መልካም ነው፤
እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው
ጽንፈኝነትን ያስወግዳል[ሀ]።

[19]በአንድ ከተማ ካሉ ዐሥር ገዦች ይልቅ፣
ጥበብ ጠቢቡን ሰው ኀያል
ታደርገዋለች።

[20]ትክክለኛውን ነገር የሚያደርግና ፈጽሞ
ኀጢአት የማይሠራ፣
ጻድቅ ሰው በምድር ላይ የለም።

[21]የሚነገረውን ቃል ሁሉ ለማዳመጥ አትሞክር፤
አለበለዚያ አገልጋይህ ሲረግምህ ትሰማ
ይሆናል፤
[22]ብዙ ጊዜ አንተ ራስህ፣
ሌሎችን እንደረገምህ ልብህ ያውቃልና

[23]እኔም ይህን ሁሉ በጥበብ ፈተኜ፣

"ጠቢብ ለመሆን ቈርጫለሁ" አልሁ፤
ይህ ግን ከእኔ የራቀ ነበር።
[24]ጥበብ ምንም ይሁን ምን፣
እጅግ ጥልቅና ሩቅ ነው፤
ማንስ ሊደርስበት ይችላል?
[25]ስለዚህ ጥበብንና የነገሮችን አሠራር
ለመመርመርና ለማጥናት፣
የክፋትን መጥፎነት፣
የሞኝነትንም እብደት ለማስተዋል፣
አእምሮዬን መለስሁ።

[26]ልቧ ወጥመድ፣
እጆቿም እግር ብረት የሆኑ፣
አሽክላ የሆነች፣
ከሞት የከፋችዋን ሴት አገኘሁ፤
እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ ከእጇ ያመልጣል፤
ኀጢአተኛውን ግን አጥምዳ ትይዘዋለች።

[27]ሰባኪው[ለ] እንዲህ ይላል፤ "እነሆ፤ መርምሬ ያገኘሁት ነገር ይህ ነው፤

"የነገሮችን ብልኀት መርምሮ ለማግኘት፣
አንዱን በአንዱ ላይ በመጨመር፣
[28]ገና በመመርመር ላይ ሳለሁ፣
ግን ያላገኘሁት፣
ከሺህ ወንዶች መካከል አንድ ቅን ሰው
አገኘሁ፣
በእነዚያ ሁሉ መካከል ግን አንዲት ቅን
ሴት አላገኘሁም።
[29]ይህን አንድ ነገር ብቻ አገኘሁ፤
እግዚአብሔር ሰውን ቅን አድርጎ
መሥራቱን፣
ሰዎች ግን ውስብስብ ዘዴ ቀየሱ።"

**8** ነገሮችን መግለጽ የሚችል፣
እንደ ጠቢብ ያለ ሰው ማን ነው?
ጥበብ የሰውን ፊት ታበራለች፤
የከበደ ገጽታውንም ትለውጣለች።

### ንጉሥን ታዘዝ

[2]በእግዚአብሔር ፊት መሐላ ስለ ፈጸምህ፣ የንጉሥን ትእዛዝ አክብር እልሃለሁ። [3]ከንጉሥ ፊት ተጣድፈህ አትውጣ፤ የወደደውንም ማድረግ ስለሚችል ለጥፋት አትሰለፍ። [4]የንጉሥ ቃል በላይ ስለ ሆነ እርሱን፣ "ምን ታደርጋለህ?" ማን ሊለው ይችላል?

[5]እርሱን የሚታዘዝ ሁሉ አይጐዳም፤
ጥበበኛም ልብ ትክክለኛውን ጊዜና
ተገቢውን አሠራር ያውቃል።
[6]የሰው መከራ እጅግ ቢጫነውም፣
ለሁሉም ነገር ትክክለኛ ጊዜና ተገቢ
አሠራር አለው።

[7]ሰው የወደፊቱን ስለማያውቅ፣
ሊመጣ ያለውን ማን ሊነግረው ይችላል?
[8]ሰው ነፋስን መቈጣጠር አይችልም[ሐ]፤
በዕለተ ሞቱም ላይ ሥልጣን ያለው ማንም
የለም፤
በጦርነት ጊዜ ማንም ከግዴታ ነጻ

7፥15 ኢዮ7፥7፤ 21፥7፤መክ8፥12-14፤ኤር12፥1
7፥17 ኢዮ15፥32
7፥18 መክ 3፥14
7፥19 ምሳ8፥14፤ መክ2፥13
7፥20 2ዜና6፥36፤ ኢዮ4፥17፤መዝ14፥3፤ ምሳ20፥9፤ሮሜ3፥12
7፥21 ምሳ30፥10
7፥23 መክ1፥17
7፥24 ኢዮ28፥12
7፥25 ኢዮ28፥3፤ መክ1፥17
7፥26 ዘፀ10፥7፤መሳ 14፥15፤ምሳ2፥16-19፤ 5፥3-5፤7፥23፤22፥14
7፥27 መክ1፥1
7፥28 1ነገ11፥3
8፥3 መክ10፥4
8፥4 አስ1፥19
8፥6 መክ3፥1

[ሀ]18 *ወይም ሁለቱንም ይከተላቸዋል*
[ለ]27 *ወይም የጉባኤ መሪ*
[ሐ]8 *ወይም መንፈሱን ለማቈየት አይችልም*

7፥15 *ጻድቅ ... ሲጠፋ፤* ጽድቅ፣ ከመከራ ወይም ያለ ወቅቱ ከመሞት ላይከላከልልን ይችላል።

7፥16 *እጅግ ጻድቅ፣ ... እጅግም ጠቢብ አትሁን፤* እውነተኛው ጽድቅና ጥበብ ከጥፋት የማያድን ከሆነ፣ የሥርዐት ጽድቅና ጥበብ ለማንም እንደማይጠቅም ግልጽ ነው።

7፥17 *እጅግ ክፉ አትሁን፤* ከመጠን ያለፈ ክፋት አጉል ድፍረት ነው፤ ጥፋትንም ያስከትላል።

7፥18 *አንዱን ... ሌላውንም፤* እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው በጽድቅና በጥበብ የሚመራ ወግ አጥባቂነትንና ሥርዐተ አልበኛነትን በማስወገድ ሚዛናዊ ሕይወት ይኖረዋል።

7፥20 *ጻድቅ ሰው በምድር ላይ የለም፤* ዐቢይ መጽሐፍ ቅዱሳዊ እውነት ነው (ሮሜ3፥10-20)።

*7፥24፤* ኢዮ 28፥12-28፤ 1ቆሮ 2፥9-16 ይመ።

*7፥26፤* ምሳ 7፥6-27 ይመ።

7፥27 *ሰባኪው፤* የ1፥1 ማብ ይመ። *የነገሮችን ብልኀት መርምሮ ለማግኘት አንዱን በአንዱ ላይ በመጨመር፤* እንደ ዚህ ዐይነቱ አካሄድ መቆሚያ የለውም፤ የምናየውን ሁሉ አስተማማኝ በሆነ ሁኔታ ልንተረጕምም አንችልም (3፥11)፤ የሰው ጥበብና መረዳት፣ ለተገለጠው እውነት ሁልጊዜ የሚገዛ መሆን አለበት።

7፥29 *እግዚአብሔር ሰውን ቅን አድርጎ መሥራቱን ... ግን፤* ዘፍ 3፥1-6፤ ሮሜ 5፥12 ይመ።

8፥2 *መሐላ ስለ ፈጸምህ፤* ለንጉሥ ታማኝ ሆኖ ለመገኘት ነው (1ዜና 29፥24 ይመ)። *የንጉሥን ትእዛዝ፤* መመሪያ ማውጣት (ቊ2) እና መመሪያውን በጥንቃቄ ማክበር (ቊ3-6) ለነጻነታችን ወሳኞች ናቸው።

8፥4 *"ምን ታደርጋለህ?" ማን ሊለው ይችላል?* ከኢሳ 45፥9፤ ከሮሜ 9፥20 ጋር ያነጻጽሩ።

8፥6 *የሰው መከራ፤* ሰው ከመከራው ይልቅ የንጉሡን ትእዛዝ አክብሮ ማየት አለበት።

8፥7-8 *ሰው ... ስለማያውቅ፣... ነፋስን መቈጣጠር አይችልም፤* መዝ3፥15፤ 2ቆሮ5፥1-10፤ ያዕ 4፥13-16 ይመ።

እንደማይሆን፣
ክፋትም የሚለማመዷትን አትለቃቸውም።

[9]ከፀሓይ በታች የተሠራውን ሁሉ በአእምሮዬ መርምሬ፣ ይህን ሁሉ አየሁ። ሰው ሰውን ለመጕዳት ገዥ የሚሆንበት ጊዜ አለ። [10]እንዲሁም ወደ ቅዱሱ ስፍራ ይመጡና ይሄዱ የነበሩት ክፉዎች ተቀብረው አየሁ፤ ይህን ባደረጉበት ከተማም ይመሰገኑ ነበር[+]፤ ይህም ደግሞ ከንቱ ነው።

[11]በወንጀል ላይ ባፋጣኝ ፍርድ ካልተሰጠ፣ የሰዎች ልብ ክፉን በማድረግ ዕቅድ ይሞላል። [12]ኀጥእ መቶ ወንጀል ሠርቶ ዕድሜው ቢረዝምም፣ እግዚአብሔርን የሚያከብሩ፣ ፈሪሀ እግዚአብሔር ያላቸው ሰዎች መልካም እንደሚሆንላቸው ዐውቃለሁ። [13]ነገር ግን ክፉዎች እግዚአብሔርን ስለማይፈሩ መልካም አይሆንላቸውም፤ ዕድሜያቸው እንደ ጥላ አይረዝምም።

[14]በምድር ላይ የሚከሠት ሌላም ከንቱ ነገር አለ፤ ጻድቃን ለክፉዎች የሚገባውን፣ ክፉ ሰዎችም ለጻድቃን የሚገባውን ይቀበላሉ፤ ይህም ደግሞ ከንቱ ነገር ነው አልሁ። [15]ለሰው፣ ከፀሓይ በታች ከመብላት፣ ከመጠጣትና ከመደሰት ሌላ የተሻለ ነገር ስለ ሌለ፣ በሕይወት ደስ መሰኘት መልካም ነው አልሁ፤ ስለዚህ እግዚአብሔር ከፀሓይ በታች በሰጠው የሕይወት ዘመኑ ሁሉ በሥራው ደስታ ይኖረዋል።

[16]ጥበብን ለማወቅና ሌት ተቀን እንቅልፍ የማያውቀውን በምድር ያለውን የሰውን ድካም ለመገንዘብ በአእምሮዬ ስመረምር፣ [17]እግዚአብሔር ያደረገውን ሁሉ አየሁ። ከፀሓይ በታች የሚደረገውን ማንም ሊያውቅ አይችልም፤ ሰው ለመመርመር ብዙ ቢጥርም፣ ትርጕሙን ማግኘት አይችልም፤ ጠቢብም እንኳ ዐውቀዋለሁ ቢል፣ ፈጽሞ ሊገነዘበው አይችልም።

## የሁሉም የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ

**9** ስለዚህ ይህን ሁሉ በልቤ አስቤ እንዲህ አልሁ፤ ጻድቃንና ጠቢባን፣ የሚሠሩትም ሥራ በእግዚአብሔር እጅ ነው፤ ነገር ግን ፍቅር ይሁን ወይም ጥላቻ የሚጠብቀውን ማንም አያውቅም። [2]ጻድቃንና ኀጥአን፣ ደጎችና ክፉዎች[◊]፣ ንጹሓንና ርኩሳን፣ መሥዋዕት የሚያቀርቡና የማያቀርቡ የሁሉም የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ አንድ ነው።

ለደጉ ሰው እንደ ሆነው ሁሉ፣
ለኀጢአተኛውም እንዲሁ ነው፤
ለሚምሉት እንደ ሆነው ሁሉ፣
መሐላን ለሚፈሩትም እንዲሁ ነው።

[3]ከፀሓይ በታች በሁሉም ላይ የሚሆነው ክፋት ይህ ነው፤ የሁሉም የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ አንድ ነው። በዚህም ላይ የሰዎች ልብ በክፋት የተሞላ ነው፤ በሕይወት እያሉም በልባቸው ውስጥ እብደት አለ፤ በመጨረሻም ወደ ሙታን ይወርዳሉ። [4]በሕያዋን መካከል ያለ ማንኛውም ሰው ተስፋ አለው[+]፤ በሕይወት ያለ ውሻ ከሞተ አንበሳ ይሻላልና!

[5]ሕያዋን እንደሚሞቱ ያውቃሉና፤
ሙታን ግን ምንም አያውቁምና፤
መታሰቢያቸው ይረሳል፤
ምንም ዋጋ የላቸውም።
[6]ፍቅራቸው፣ ጥላቻቸው፣
ቅናታቸውም ከጠፋ ቈይቶአል፤
ከፀሓይ በታች በሚሆነው ነገር ሁሉ፣
ፈጽሞ ዕጣ ፈንታ አይኖራቸውም።

[7]ሂድ፤ ምግብህን በደስታ ብላ፤ ወይንህንም ልብህ ደስ ብሎት ጠጣ፤ ባደረግኸው ነገር እግዚአብሔር ደስ ብሎታልና። [8]ዘወትር ልብስህ ንጭ ይሁን፤ ራስህንም ዘወትር በዘይት ቅባ። [9]እግዚአብሔር ከፀሓይ በታች በሰጠህ በዚህ ትርጕም የለሽ የሕይወት ዘመን ሁሉ፣ ከንቱ በሆኑትም ቀኖችህ ሁሉ ከምትወዳት ሚስትህ ጋር ደስ ይበልህ፤ በሕይወትህና ከፀሓይ በታች በምትደክምበት ነገር ሁሉ ይህ ዕድል ፈንታህ ነውና። [10]እጅህ የሚያገኘውን ሥራ ሁሉ በሙሉ ኀይልህ ሥራው፤ ልትሄድበት ባለው መቃብር[‡] ውስጥ መሥራትም ሆነ ማቀድ፣ ዕውቀትም ሆነ ጥበብ የለምና።

8፥10 መክ1፥11
8፥12 ዘፀ1፥20፤ ዘዳ12፥28፤መክ3፥14
8፥13 ዘዳ4፥40፤ ኢዮ5፥26፤መዝ 34፥12፤መክ3፥14፤ ኢሳ65፥20
ኢዮ21፥7፤መክ7፥15
8፥15 ዘፀ32፥6፤መዝ 42፥8፤መክ2፥1፡3
8፥16 መክ1፥13፡17
8፥17 ኢዮ28፥3 ፡23፤ሮሜ11፥33
9፥1 መክ10፥14
9፥2 ኢዮ9፥22፤ መክ2፥14
9፥3 ኢዮ9፥22፤ 21፥26፤መክ2፥14፤ ኤር11፥8፤13፥10፤ 16፥12፤17፥9
9፥5 ኢዮ14፥21፤ መዝ9፥6፤መክ1፥11
9፥6 ኢዮ21፥21
9፥7 ዘኍ6፥20፥ መክ2፥24
9፥8 ራእ 3፥4
9፥9 ኢዮ31፥2፤ ምሳ5፥18
9፥10 ዘኍ16፥33፤ 1ሳሙ10፥7፤መዝ 6፥5፤መክ2፥24፤11፥6 ፤ኢሳ38፥18

[+]10 አንዳንድ የዕብራይስጥ ቅጆችና ሰብዓ ሊቃናት (አቍዊላ) እንዲሁ ሲሆኑ አብዛኞቹ የዕብራይስጥ ቅጆች ግን ተረስተዋል ይላሉ።
[◊]2 ሰብዓ ሊቃናት (አቍዊላ) ቩልጌትና ሱርስት እንዲሁ ሲሆኑ ዕብራይስጡ ግን ክፉዎች የሚለው የለም
[+]4 ወይም ታዲያ የሚመረጠው ምንድነው? ለሕያዋን ሁሉ ተስፋ አለ
[‡]10 በዕብራይስጥ ሲኦል ማለት ነው

8፥10 *ክፉዎች ተቀብረው፤* ይህ ዐውደ ምንባብ ለክፉዎች ስለማይገባ ክብር ይናገራል (የ6፥3 ማብ ይመ፤ ከኢዮ 21፥28-33፤ ከሉቃ 16፥22 ጋር ያነጻጽሩ)።

*8፥11፤* የዘገየ ቅጣት የበለጠ ስህተት እንዲፈጸም ይገፋፋል።

8፥12 *ዐውቃለሁ፤* እዚህ ላይ ሰባኪው ገና በመመርመር ላይ እንዳለ ግን እንዳላገኘ ሰው ሳይሆን (7፥28) ከጽኑ እምነት የተነሣ ይናገራል። ለተመሳሳይ አገላለጽ 3፥17፤11፥9፤12፥14 ይመ።

*8፥14፤* ኢዮ 21-24 ላይ ይህን ሐሳብ በስፋት ያብራራል፤ መዝ 73 ሐሳቡ የሚያስከትለውን ከፍተኛ ስሜት ያሳያል፤ ዮሐ 5፥28-29 ደግሞ የመጨረሻውን ማብራሪያ ይሰጣል።

8፥15 *ከመብላትና ከመጠጣትና ከመደሰት፤* ከጊዜያዊ ምቾት አንጻር የተነገረ ነው (5፥19፤9፥7፤ ዘዳ 8 ይመ)። ይህ እንዲሁም በሉቃ 12፥19-20፤ 1ቆሮ 15፥32 ይመ።

8፥17 *ማንም ሊያውቅ አይችልም፤* እንድናውቅ የተፈቀደልንና ያልተፈቀደልን ነገር በዘዳ29፥29 ላይ ተመልክቶአል።

9፥1 *ፍቅር ይሁን ወይም ጥላቻ፤* ወደ ፊት የሚሆነው ነገር ሁሉ በእግዚአብሔር እጅ ነው። የወደፊቱ መልካም ይሁን ወይም አይሁን የሚያውቅ ሰው የለም።

9፥2 *የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ አንድ ነው፤* ጠቢቡና ሞኙ ብቻ ሳይሆኑ (2፥14)፣ ደጉና ክፉውም ሰው መጨረሻቸው አንድ እንደ ሆነ በ3፥20 ላይ ተመልክቶአል። በመጨረሻ እግዚአብሔር ለተደረገው ነገር ተገቢ ፍርድ እንደሚሰጥ ሰባኪው እርግጠኛ ለመሆኑ የ8፥12 ማብ ይመ።

9፥3 *ክፋት ... በክፋት፤* የጻድቁና የኀጥኡ በሞት አንድ መሆን አንዳንድ ሰዎችን ኀጢአት እንዲሠሩ ያደፋፍራቸዋል።

9፥5 *ምንም ዋጋ የላቸውም፤* የሞቱ ሰዎች በምድራዊ ሕይወት ለመደሰትና በድካማቸው ፍሬ ለመጠቀም ዕድል የላቸውም።

*9፥7፤* የ8፥15 ማብ ይመ።

*9፥10፤* ከቈላ 3፥23 ጋር ያነጻጽሩ።

[11]ሌላም ነገር ከፀሐይ በታች አየሁ፦
ሩጫ ለፈጣኖች፣
 ውጊያም ለኀያላን አይደለም፤
እንጀራ ለጥበበኞች፣
 ወይም ባለጠግነት ለብልኆች፣
ወይም ሞገስ ለዐዋቂዎች አይሆንም፤
 ጊዜና ዕድል ግን ሁሉን ይገናኛቸዋል።
[12]ደግሞም የራሱን ጊዜ የሚያውቅ ሰው የለም፤
ዓሦች በክፉ መረብ እንደሚያዙ፣
 ወይም ወፎች በወጥመድ
 እንደሚጠመዱ፣
ሰዎችም ሳያስቡት በሚመጣባቸው፣
 በክፉ ጊዜ ይጠመዳሉ።

**ጥበብ ከሞኝነት ይበልጣል**

[13]እንዲሁም እጅግ ያስገረመኝን ይህን የጥበብ ምሳሌ ከፀሐይ በታች አየሁ፦ [14]ጥቂት ሰዎች የሚኖሩባት አንዲት ትንሽ ከተማ ነበረች፤ አንድ ኀያል ንጉሥም መጣባት፤ ከበባት፤ በላይዋም ትልቅ ምሽግ ሠራባት። [15]በዚያችም ከተማ ጥበበኛ የሆነ አንድ ድኻ ሰው ይኖር ነበር፤ በጥበቡም ከተማዋን አዳናት፤ ነገር ግን ያን ድኻ ማንም አላስታወሰውም። [16]ስለዚህ፣ "ጥበብ ከኀይል ይበልጣል" አልሁ፤ ሆኖም የድኻው ጥበብ ተንቆአል፤ ቃሉም አልተሰማም።
[17]ሞኞችን ከሚያስተዳድር ገዥ ጩኸት
 ይልቅ፣
 ጠቢብ በዝግታ የሚናገረው ቃል
 ይደመጣል።
[18]ጥበብ ከጦር መሣሪያ ይበልጣል፤
 ነገር ግን አንድ ኀጢአተኛ ብዙ መልካም
 ነገርን ያጠፋል።

# 10

የሞቱ ዝንቦች ሽቶን
 እንደሚያገሙ፣
 ትንሽ ሞኝነትም ጥበብንና ክብርን
 ያቀላል።
[2]የጠቢብ ልብ ወደ ቀኝ፣
 የሞኝ ልብ ግን ወደ ግራ ያዘነብላል።
[3]ሞኝ በጐዳና ሲሄድ ማስተዋል ይጐድለዋል፤
 ጅል መሆኑንም ለማንም ይገልጻል።
[4]የገዥ ቍጣ በተነሣብህ ጊዜ፣
 ስፍራህን አትልቀቅ፤
 ትዕግሥት ታላቀን ጥፋት ጸጥ ያደርጋልና።
[5]ከፀሐይ በታች ያየሁት ክፉ ነገር አለ፤
 ይህም ከገዥ የሚወጣ ስሕተት ነው፤
[6]ሞኞች በብዙ የክብር ስፍራዎች ሲቀመጡ፣
 ሀብታሞች ግን በዝቅተኛ ስፍራ ሆነዋል።
[7]መሳፍንት እንደ ባሮች በእግራቸው ሲሄዱ፣
 ባሮች ፈረስ ላይ ተቀምጠው አይቻለሁ።
[8]ጕድጓድን የሚምስ ራሱ ይገባበታል፤
 ቅጥርንም የሚያፈርስ እባብ ይነድፈዋል።
[9]ድንጋይ የሚፈነቅል ይጐዳበታል፤
 ግንድንም የሚፈልጥ አደጋ ላይ መውደቁ
 አይቀርም።
[10]መጥረቢያ ቢደንዝ፣
 ጫፉም ባይሳል፣
 በዙ ጕልበት ይጨርሳል፤
 ብልኀት ግን ለውጤት ያበቃል።
[11]እባብ በድግምት ከመፍዘዙ በፊት ቢነድፍ፣
 ለደጋሚው ምንም አይጠቅመውም።
[12]ከጠቢብ አፍ የሚወጣ ቃል ባለ ሞገስ ነው፤
 ሞኝ ግን በገዛ ከንፈሩ ይጠፋል፤
[13]ቃሉ በመጀመሪያ ሞኝነት ነው፤
 በመጨረሻም ደግሞ ክፉ እብደት ነው፤
[14] ሞኝም ቃልን ያበዛል።
የሚመጣውን የሚያውቅ የለም፤
 ከእርሱ በኋላ የሚሆነውንስ ማን ሊነግረው
 ይችላል?
[15]የሞኝ ሥራ ራሱን ያደክመዋል፤
 ወደ ከተማ የሚወስደውንም መንገድ
 አያውቅም።
[16]አንቺ፣ ንጉሥሽ ልጅ[1] የሆነ፣
 መሳፍንትሽም በጠዋት ግብዣ የሚያደርጉ
 ምድር ሆይ፤ ወዮልሽ!
[17]አንቺ ንጉሥሽ ከተከበረው ዘር የሆነ፣
 ለመስከር ሳይሆን ለብርታት፣
 በተገቢው ጊዜ የሚበሉ መሳፍንት ያሉሽ
 ምድር ሆይ፤ የተባረክሽ ነሽ፤
[18]ሰው ሰነፍ ከሆነ ጣራው ይዘብጣል፤
 እጆቹም ካልሠሩ ቤቱ ያፈሳል።

9፥11 ዘዳ8፥18፤ኢዮ32፥13፤መክ2፥14፤ኢሳ47፥10፤ኤር9፥23፤አሞ2፥14-15
9፥12 መዝ73፥22፤መሳ29፥6፤መክ2፥14
9፥13 2ሳሙ20፥22
9፥15 ዘፍ40፥14፤መክ1፥11
9፥16 አስ6፥3
9፥18 መክ2፥13
10፥1 ምሳ13፥16፤18፥2
10፥3 ምሳ13፥16
10፥4 መክ8፥3፤ምሳ16፥14
10፥6 ምሳ29፥2
10፥7 ምሳ19፥10
10፥8 አስ2፥23፤መዝ9፥16፤57፥6፤አሞ5፥19
10፥9 ምሳ26፥27
10፥11 መዝ58፥5፤ኢሳ3፥3
10፥12 ምሳ10፥6፡32፤14፥3፤15፥2፤18፥7
10፥14 መክ5፥3፤9፥1
10፥16 ኢሳ3፥4-5፡12
10፥17 ዘዳ14፥26፤1ሳሙ25፥36፤ምሳ31፥4
10፥18 ምሳ20፥4፤24፥30-34

[1]16 *ወይም አሽከር*

9፥11 *ጊዜና ዕድል፤* ማን እንደሚሳካለት እርግጠኛ መሆን አይቻልም፤ ይህም ሁነቶች ሁሉ በሰው ቍጥጥር ሥር አለመሆናቸውን ያረጋግጣል።
9፥12 *ጊዜ፤* የመከራና የጥፋት ጊዜ ነው። *ሰዎችም ... ይጠመዳሉ፤* ማንም ሰው መቼ እንደሚያሸንፍ ወይም መቼ እንደሚሸነፍ ማወቅ ስለማይችል፣ አስቀድሞ ድል አደርጋለሁ ብሎ መናገር አስቸጋሪ ነው።
9፥15 *ነገር ግን ... ማንም አላስታወሰውም፤* ሰው በራሱ ጥበብ ከመጠን በላይ እንዳይመካ የተሰጠ ተጨማሪ ማስጠንቀቂያ ነው። የሰው ጥበብ ታላቅነት ይደበዝዛል፣ መልካምነቱም ይበላሻል (ቍ 18) ለሞትም መፍትሔ የለውም (2፥15-16)።
10፥1 *ትንሽ ሞኝነትም ... ያቀላል፤* በ2ነገ 20፥12-19 ላይ የተገለጸው ታሪክ ለዚህ ጥሩ ምሳሌ ነው።
10፥2 *ወደ ቀኝ ... ወደ ግራ፤* ብዙ ወይም ጥቂት በጎነትን የሚያመለክት ነው (ከዘፍ48፥13-20 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ወይም በአይሁድ ሥነ ጽሑፍ ውስጥ እንደ ተጠቀሰው፣ ጥሩና መጥፎ የሆነውን ነገር የሚያመለክት ነው።
10፥5 *ከገዥ ... ስሕተት፤* ሰባኪው በሰው አስተዳደር ውስጥ የተመለከተውን ነገር ለማስተዋል ቍ 4፡6-7፡16-17፡20፤ 3፥16፤ 4፥1-3፡13-16፤ 5፥8-9፤ 8፥2-6፡ 10፣11፤9፥17 ይመ።
10፥12 *ቃል፤* በቅኔ መጻሕፍት ውስጥ ተደጋግሞ ተጠቅሶአል (ምሳ 15 ይመ)።
10፥15 *ወደ ከተማ የሚወስደውንም መንገድ አያውቅም፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ሞኝ የሚባለው የእግዚአብሔርን ቃል ለመማር የማይፈልግ ሰው ሲሆን (የ5፥4 ማብ ይመ)፣ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ምሳሌያዊ አባባል ግን ከዚህ የከፋ ትርጕም ያለውን ያመለክታል።
10፥16 *ንጉሥሽ ልጅ የሆነ፤* በ4፥13 ላይ እንደ ተጠቀሰው "ጠቢብ የሆነ ድኻ ወጣት" ሳይሆን፣ ያለ ድካም የከበረውና ደካማ አስተሳሰብ ያለውን አምባገነን ንጉሥ ያሳያል፤ ያለ አግባብ ሥልጣን ላይ በመውጣት ለአጭር ጊዜ እስራኤልን ስለ ገዙትና ለውድቀት ስለዳረጉት አረማውያን ነገሥታት በ2ነገ 15፥8-15፤ በሆሴ 7፥3-7 ይመ።
10፥18 *ሰነፍ ... እጆቹም ካልሠሩ፤* የ4፥5 ማብ ይመ።

[19]ግብዣ ለሣቅ ያዘጋጃል፤
ወይንም ሕይወትን ያስደስታል፤
ገንዘብም ካለ ሁሉ ነገር አለ።

[20]በሐሳብህም እንኳ ንጉሥን አትንቀፍ፤
በመኝታ ክፍልህም ባለጠጋን
አትርገም፤
የሰማይ ወፍ ቃልህን ልትወስድ፣
የምትበረዋም ወፍ የምትለውን
ልታደርስ ትችላለችና።

**እንጀራ በውሃ ላይ**

**11** እንጀራህን በውሃ ላይ ጣል፤
ከብዙ ቀን በኋላ መልሰህ
ታገኘዋለህና።
[2]ሀብትህን ሰባት ቦታ፣ እንዲያውም ስምንት
ቦታ ከፍለህ አስቀምጥ፤
በምድሪቱ ላይ የሚመጣውን ጥፋት
አታውቅምና።

[3]ደመናት ውሃ ካዘሉ፣
በምድር ላይ ዝናብን ያዘንባሉ፤
ዛፍ ወደ ደቡብም ሆነ ወደ ሰሜን ቢወድቅ፣
በወደቀበት ቦታ በዚያ ይጋደማል።
[4]ነፋስን የሚጠባበቅ አይዘራም፤
ደመናትንም የሚያይ አያጭድም።

[5]የነፋስን መንገድ እንደማታውቅ፣
ሕይወት ወይም መንፈስ በእናት ማሕፀን
ውስጥ ወደሚገኘው አካል እንዴት
እንደሚገባ[a] እንደማታውቅ ሁሉ፣
ሁሉን ሠሪ የሆነውን፣ የእግዚአብሔርን ሥራ
ማስተዋል አትችልም።

[6]ጠዋት ላይ ዘርህን ዝራ፤
ማታም ላይ እጅህ ሥራ አይፍታ፤
ይህ ወይም ያ፣
ወይም ሁለቱ መልካም ይሁኑ፣
የቱ እንደሚያፈራ አታውቅምና።

**ወጣት ሳለህ ፈጣሪህን አስብ**

[7]ብርሃን መልካም ነው፤
ፀሐይንም ማየት ለዐይን ደስ ያሰኛል።

10፥19 ዘፍ14፥18፤ መሳ9፥13
10፥20 ዘፀ22፥28
11፥1 ቍ6፤ዘዳ 24፥19፤ኢሳ32፥20 ፤ሆሴ10፥12
11፥5 ዮሐ3፥8-10፤ መዝ139፥14-16፤
11፥6 መክ9፥10
11፥7 መክ7፥11
11፥8 መክ12፥1
11፥9 አዮ19፥29፤ መክ2፥24፤3፥17
11፥10 መዝ94፥19፤ መክ2፥24
12፥12 ሳሙ19፥35፤ መክ11፥8
12፥4 ኤር25፥10
12፥5 ኢዮ10፥21፤ ኤር9፥17፤አሞ5፥16

[8]ሰው ምንም ያህል ብዙ ዓመት ቢኖር፣
በእነዚህ ሁሉ ይደሰት፤
ነገር ግን ጨለማዎቹንም ቀናት ያስብ፤
እነርሱ ይበዛሉና፤
የሚመጣውም ነገር ሁሉ ከንቱ ነው።

[9]አንተ ወጣት በወጣትነትህ ጊዜ ደስ ይበልህ፤
በወጣትነትህም ዘመን ልብህ ደስ ያሰኝህ፤
የልብህን መንገድ፣
ዐይንህ የሚያየውንም ሁሉ ተከተል።
ነገር ግን ስለ እነዚህ ነገሮች ሁሉ፣
እግዚአብሔር ወደ ፍርድ እንደሚያመጣህ
ዕወቅ።
[10]ስለዚህ ጭንቀትን ከልብህ አርቅ፤
ክፉ ነገርንም ከሰውነትህ አስወግድ፤
ወጣትነትና ጕብዝና ከንቱ ናቸውና።

**12** የጭንቀት ጊዜ ሳይመጣ፣
"ደስ አያሰኙኝም"
የምትላቸው ዓመታት ሳይደርሱ፣
በወጣትነትህ ጊዜ፣
ፈጣሪህን አስብ።
[2]ፀሐይና ብርሃን፣
ጨረቃና ከዋክብት ሳይጨልሙ፣
ደመናትም ከዝናብ በኋላ ሳይመለሱ፣
[3]ቤት ጠባቂዎች ሲርዱ፣
ብርቱዎች ሲጕበጡ፣
ጥቂት በመሆናቸው ፈጪታዎች ሲያቆሙ፣
በመስኮት የሚያዩትም ሲፈዙ፣
[4]ወደ አደባባይ የሚያወጡ በሮች ሲዘጉ፣
ወፍጮ ሚልጠ ድምፁ ሲላሽ፣
ሰው በወፍ ድምፅ ሲነሣ፣
ዝማሬው ሁሉ ሲደክም፣
[5]ዳገት መውጣት ሲያርድ፣
መንገድም ሲያስፈራ፣
የለውዝ ዛፍ ሲያብብ፣
አንበጣም ራሱን ሲጐትት፣
ፍላጎት ሲጠፋ፤
በዚያን ጊዜ ሰው ወደ ዘላለማዊ ቤቱ ይሄዳል፤

[a]5 ወይም አካል በእናት ማሕፀን ውስጥ እንዴት እንደሚሠራ እንደማታውቅ ሁሉ፣

10፥19 *ገንዘብም ካለ ሁሉ ነገር አለ፤* ይህ ዐረፍተ ነገር የተለያየ ትርጕም ሊይዝ ይችላል፤ ይኸውም ስለ ሰው የተሰጠ መጥፎ አስተያየትን፣ ወይም ከረጅም ዕድሜ ይልቅ መልካም ኑሮ እንደሚሻል የተሰጠ ምክርን ወይም ከገንዘብ የሚገኝ ከፍተኛ ጥቅምን የሚያመለክት ይሆናል (ከሉቃ 16፥9 ጋር ያነጻጽሩ)።

11፥1 *እንጀራህን በውሃ ላይ ጣል፤* ሁልጊዜ ላለመጎዳት ጥንቃቄ ማድረግ ብቻ ሳይሆን (ምሳ11፥24 ይመ)፣ አደጋን ተጋፍጠው በባሕር ላይ ንግድ እንደሚጠቀሙ ሰዎች ቈራጥ እርምጃ መውሰድ አስፈላጊ እንደ ሆነ ያመለክታል።

11፥2 *ሀብትህን ሰባት ቦታ ... ከፍለህ፤* ያልተጠበቀ አደጋ ደርሶብህ የሌሎችን ርዳታ የምትሻበት ጊዜ ሊኖር ስለሚችል፣ ሀብት ባለህ ጊዜ ለተቸገሩት አካፍል።

11፥3-6 *ደመናት ... ዛፍ ... ነፋስን ... ዘርህን፤* ሊሆን ይችላል፤ ወይም ሳይሆን አልቀረም እያልህ አንድን ነገር ያዝ ለቀቅ አታድርግ፤ ከምታውቀውና ልታደርግ ከምትችለው ቦታ ላይ ጀምር፤ ያንተ ድርሻ ወይም ዕውቀት ውሱን መሆኑን አስተውል።

11፥5 *የነፋስን፤* ከዮሐ 3፥8 ጋር ያነጻጽሩ (በሁሉም ጥቅሶች ውስጥ "ነፋስ" እና "መንፈስ" አንድ ዐይነት ትርጕም አላቸው)።

*11፥7-10፤* ሕይወትን እጅግ በጣም በተሟላ ሁኔታ መምራት አስፈላጊ እንደ ሆነ ያሳስባል።

11፥8-10 *ከንቱ፤* በቍ 7-10 ላይ የተጠቀሱት አስደናቂ ስጦታዎች ዐይናችንን እንዳያሳውሩና እንዳያሳስቱን ያስጠነቅቃል፤ ቍ 9 ወደ ትክክለኛው መንገድ ይመራናል።

11፥9 *ወደ ፍርድ፤* 12፥14 እና ማብ ይመ። ከእግዚአብሔር ዘንድ ሽልማት ወይም ቅጣት መኖሩ እያንዳንዱ የሕይወት ጕዞ ዋጋ እንዳለው እንጂ ከንቱ መሆኑን አያመለክትም፤ ይህን ማወቅም ለልባችን ምሪት ይሆናል፤ በዐይናችንም አጥርተን እንድናይ ይረዳናል። ይህ አካሄድ ለም12 የተመቻቸ ሁኔታን ይፈጥራል።

*12፥2-5፤* የሰው የኑሮ ሁኔታ እየተበላሸ እንደሚሄድ የሚያሳይ ሥዕላዊ መግለጫ ነው፤ የማርጀትንም ሁኔታ በንጽጽር ያመለክታል።

12፥3 *ቤት ጠባቂዎች፤* ይህ ሐረግና ሌሎች ተለዋጭ ዘይቤዎች የሰውነት ክፍሎችን ሳያመለክቱ አይቀርም። ነገር ግን ምስያውን ለመጠቀም ብቻ ሲባል ጨለማን፣ ማእበልን፣ ሊወድቅ ያዘመመን ቤት፣ ባዶ የቀረ የውሃ ጕድጓድንና የመሳሰሉትን (ቍ5) ዘይቤያዊ አገላለጽ አደናቅፎ የቅኔውን ውበት ማበላሸት አይገባም።

12፥5 *የለውዝ ዛፍ፤* በላዩ ላይ ያለው የገረጣ አበባ ከእርጅና የተነሣ የሚበቅለውን ሽበት ያመለክት ይሆናል። *አንበጣም፤* በተፈጥሮው ፈጣን ነው፤ ቅዝቃዜ ባለበት ማለዳ በዝግታ መንቀሳቀሱም (ከናሆ 3፥17 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ሰውነት እንደ ልብ የማይታዘዝበትን የሽምግልና ጊዜ ያመለክታል። *ዘላለማዊ ቤቱ፤*

አልቃሾችም በአደባባዮች ይዞራሉ።

[6]የብር ሰንሰለት ሳይበጠስ፣
የወርቅ ሳሕንም ሳይሰበር፣
የውሃ መቅጃው በምንጩ አጠገብ
ሳይከሰከስ፣
ወይም መንኰራኵሩ በውሃ ጒድጓድ
ላይ ሳይሰበር፣
[7]ዐፈር ወደ መጣበት መሬት ሳይመለስ፣
መንፈስም ወደ ሰጠው ወደ እግዚአብሔር
ሳይመለስ፣
ፈጣሪህን አስብ።

[8]ሰባኪው[ⁱ] "ከንቱ! ከንቱ!
ሁሉም ነገር ከንቱ ነው!" ይላል።

### የነገሩ ፍጻሜ

[9]ሰባኪው ጥበበኛ ብቻ አልነበረም፤ ነገር ግን ለሕዝቡ ዕውቀትንም ያስተምር ነበር። እርሱም በጥልቅ አሰበ፤ ተመራመረም፤ ብዙ ምሳሌዎችንም በሥርዐት አዘጋጀ። [10]ሰባኪው ትክክለኛውን ቃል ለማግኘት ተመራመረ፤ የጻፈውም ቅንና እውነት ነበር።

[11]የጠቢባን ቃላት እንደ ሹል የከብት መንጃ ናቸው፤ የተሰበሰቡ አባባሎቹም እጅግ ተቀብቅበው እንደ ገቡ ችንካሮች ሲሆኑ፣ ከአንድ እረኛ የተሰጡ ናቸው። [12]ልጄ ሆይ፤ ከዚህ ሁሉ በላይ በማንኛውም ነገር ተጠንቀቅ፤ አንዳችም አትጨምር።

ብዙ መጻሕፍትን መጻፍ ማብቂያ የለውም፤ ብዙ ማጥናትም ሰውነት ያደክማል።

[13]እንሆ፤ ሁሉ ነገር ከተሰማ ዘንድ፤
የነገሩ ሁሉ ድምዳሜ ይህ ነው፤
እግዚአብሔርን ፍራ፤ ትእዛዛቱንም ጠብቅ፤
ይህ የሰው ሁለንተናዊ ተግባሩ ነውና።
[14]መልካምም ይሁን ክፉ፣
ስውር የሆነውን ነገር ሁሉ አንድ
ሳይቀር፣
ማንኛውንም ሥራ እግዚአብሔር ወደ
ፍርድ ያመጣዋልና።

12፥7 ዘፍ2፥7፤ ኢዮ20፥8፤መዝ 146፥4፤መክ3፥21፤
12፥8 መክ1፥1፡2
12፥9 1ነገ4፥32
12፥10 ምሳ22፥20-21
12፥11 ዕዝ9፥8፤ኢዮ 6፥25
12፥12 መክ1፥18
12፥13 ዘዐ20፥20፤ ዘዳ4፥2፡6፤1ሳሙ12፥24፤ኢዮ23፥15፤37፥24
12፥14 ኢዮ19፥29፤ 34፥21፤መዝ19፥12፤ መክ3፥17፤ኤር16፥17፤23፥24

[ⁱ]8 ወይም የጉባኤ መሪ እንዲሁም በቍ9 እና 10

ከምንባቡ አንጻር ይህ የሚያመለክተው መቃብርን እንጂ ከዚያ ባሻገር ያለውን አይደለም።

12፥6 *የብር ሰንሰለት ... የወርቅ ሳሕንም፤* በብር ሰንሰለት ተንጠልጥሎ እንደ ተሰቀለ መብራት ማለት ነው፤ ድንገት አንድ ሰው ቢሰብረው፣ ብርሃኑና ውበቱ ይጠፋል፤ የሰውም ሕይወት እንደዚሁ ፈጥኖ እንደሚጠፋ ያመለክታል።

12፥8 *ከንቱ፤* ያለ እግዚአብሔር የሆነ ከፀሓይ በታች ያለ ምድራዊ ሕይወት መጨረሻው ምን እንደሚመስል የሚያመለክት ቃል ነው፤ ነገር ግን ወደ ፈጣሪያችን ብንቀርብ (ቍ 1)፣ የእርሱም ፍርድ እርግጠኛ እንደ ሆነ ብንረዳ (11፥9)፣ ሕይወት ከንቱ አይሆንም። *ሰባኪው፤* የ1፥1 ማብ ይመ።

12፥9 *አሰበ፤ ተመራመረም፤* ሰው እውነትን ለመፈለግና ማስተዋልን ለማግኘት የተቻለውን ሁሉ በማድረግ ያሳየውን ከባድ ጥረት ያመለክታል።

12፥11 *በአንድ እረኛ የተሰጡ፤* በቍ 12 ላይ በአጽንዖት እንደ ተገለጸው የእግዚአብሔር ቃል የራሱ የሆነ የተለየ ሐሳብ እንዳለው በማሳየት የነገሩን ሌላ ገጽታ ያመለክታል።

*12፥13-14፤* ዋናውን የሰው ሕይወት መጨረሻ ያመለክታል።

12፥13 *እግዚአብሔርን ፍራ፤* በፍቅር እግዚአብሔርን ማክበር የጥበብ መሠረቱ (መዝ 111፥10፤ ምሳ 1፥7፤9፥10)፣ የጥበብ ሁለንተናው (ኢዮ 28፥28) እና መደምደሚያው ነው። *ሰው ማድረግ የሚገባው ሁሉ፤* ከንቱ ከመሆን ለመዳን አስቀድመን ማድረግ የሚገባንን ዐቢይ ጕዳይ የሚያመለክት ማለት ነው።

12፥14 *ማንኛውንም ሥራ ... ወደ ፍርድ፤* የዚህ እውነት ፍንጭ ዐልፎ ዐልፎ በመጽሐፉ ውስጥ በ3፥17፤ 8፥12-13፤ 11፥9 እና በማብራሪያው ላይ ተጠቅሶአል፤ ማቴ 12፥36፤ 1ቆሮ 3፥12-15፤ 2ቆሮ 5፥9-10፤ ዕብ 4፥12-13 ይመ። *ስውር የሆነውን ነገር ሁሉ፤* ሮሜ 2፥16 ይመ።

# ማሕልየ መሓልይ

## መግቢያ

### አሰያየሙ

በዕራይስጡ ቅጅ ላይ ለዚህ መጽሐፍ የተሰጠው ስም "የሰሎሞን ማሕልየ መሓልይ" ይላል፤ ይህም ማለት መጽሐፉ የተጻፈው በሰሎሞን ወይም ለሰሎሞን ወይም ስለ ሰሎሞን መሆኑን ያስገነዝ ባል:: "ማሕልየ መሓልይ" ማለት "ከማሕልይ የሚበልጥ ማሕልይ" (ከመዝሙሮች ሁሉ የሚበልጥ መዝ ሙር) ማለት ነው (በዘዳ10፥17 ላይ "የአማልክት አምላክና የጌቶች ጌታ"፤ በ1ጢሞ6፥15 ላይ "የነገ ሥታት ንጉሥ" ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ)::

### ጸሓፊውና የተጻፈበት ጊዜ

ቍጥር 1 የዚህ መጽሐፍ ጸሓፊ ሰሎሞን መሆኑን ያመለክታል (የቍ1፥1 ማብ ይመ፤ ሆኖም ከላይ አሰያየሙ የሚለውን ይመ):: የሰሎሞን ስም ሰባት ጊዜ ተጠቅሶአል (1፥1:5፤3፥7:9:11፤ 8፥11-12)፤ ሌሎች ብዙ ቍጥሮች ደግሞ ስለ ንጉሡ ይናገራሉ (1፥4:12፤ 7፥5):: ይሁንና ጸሓፊው ሰሎሞን ይሁን ወይም አይሁን እሁንም መልስ ያላገኘ ጥያቄ ነው::

ይህ መጽሐፍ የተጻፈው በሰሎሞን ዘመን መንግሥት በዐሥረኛው ምእተ ዓመት እንደ ሆነ መናገር ይቻላል:: ምንም እንኳ የቴርሳ መጠቀስ ግልጽ ባይሆንም፣ ቴርሳና ኢየሩሳሌም በአንድ አፍ (6፥4) መነገራቸው መጽሐፉ የተጻፈው ንጉሥ ዘምሪ (885-874 ዓ.ቅ.ክ፤ 1ነገ 16፥23-24 ይመ) ከመንገ ሡ በፊት ነው ለሚለው ሐሳብ እንደ ማስረጃ ሊጠቀስ ይችላል:: በሌላ በኩል ደግሞ ብዙዎች የመጽሐ ፉን ቋንቋ መሠረት በማድረግ እንዲህ ያለው መጽሐፍ ሊጻፍ የሚችለው ሰሎሞን ከነገሠ ከብዙ ዓመ ታት በኋላ ነው ይላሉ:: እስከ አሁን ባለው መረጃ መሠረት ግን የመጽሐፉን ቋንቋ አስመልክቶ ምንም መናገር አይቻልም::

መጽሐፉ የተጻፈው በአንድ ቋንቋ፣ ዘዬ፣ ድምፀት፣ ገለጻና አዝማች በመሆኑ፣ ጸሓፊው አንድ ሰው ነው የሚል አስተያየት ተሰንዝሯል:: ይሁን እንጂ ይህ መጽሐፍ በአንድ ሰው ወይም በተወሰነ ጊዜና ቦታ ሊጻፍ አይችልም የሚሉት ሰዎች የሚያቀርቡት ማስረጃ አላቸው ይኸውም በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ ነዋሪዎች ዘንድ በአንድ ወጥ የአጻጻፍ ስልት ተጠቅሞ መጻፍ የተለመደ ነው ይላሉ::

### ትርጓሜ

የማሕልዩን (የመዝሙሩን) መፍቻ ቁልፍ ለማግኘት የመጽሐፍ ቅዱስ ሊቃውንት የጥንት ትንቢ ቶችን፣ የጥበብና የአቡቀለምሲስ መጽሐፎችን፣ የጥንት ግብጻውያንንና ባቢሎናውያንን የፍቅር መዝሙ ሮችን፣ የሴማያውያንን የሰርግ ዘፈኖችንና የጥንት መስጴጦምያ የዘር መዝሙሮችን በጥንቃቄ መርም ረዋል:: እስከ አሁን ድረስ ለዚህ መጽሐፍ ተጓዳኝ ሆኖ የተገኘው መጽሐፈ ምሳሌ ብቻ ነው (ምሳ5፥15-20፤ 6፥24-29፤ 7፥6-23 ይመ):: በ8፥6-7 ላይ ስለ ፍቅር የተሰጠው ገለጻ (በምሳ1-9 እና ኢዮ28 ላይ ስለ ጥበብ ከተሰጠው ገለጻ ጋር ያነጻጽሩ) ይህ መጽሐፍ መደቡ ከቅዱሳት መጻሕፍት የጥበብ መጻሕፍት ተርታ እንደ ሆነ በእጅጉ ያመለክታል፤ የአገላለጽ ስልቱም ከጥበብ መጻሕፍቱ ጋር ተመሳሳይ ነው:: ጥበ ብና ፍቅር የእግዚአብሔር ስጦታ በመሆናቸው በምስጋናና በደስታ ልንቀበላቸው እንደሚገባ መጽሐፍ ቅዱስ ያስተምራል::

ይህ አስተያየት ታዲያ ማሕልዩ የሚናገረው በእግዚአብሔርና በእስራኤል መካከል ስላለው ግንኙ ነት ወይም በክርስቶስና በቤተ ክርስቲያን መካከል ስላለው ግንኙነት ወይም በክርስቶስና በነፍሶች መካ ከል ስላለው ግንኙነት ነው ከሚለው የብዙዎች አስተያየት ጋር የሚጣረስ ነው:: (እነዚህ አስተያየቶች የተሰጡት መጽሐፈ ማሕልይ በአዲስ ኪዳን ውስጥ በቀጥታም ይሁን በተዘዋዋሪ ተጠቅሶ ባልተገኘበት ሁኔታ ነው):: ከዚህ በተጨማሪ መጽሐፉ የሚያወሳው አንዲት ልጃገረድ የቀድሞ ፍቅረኛዋን (ንጉሡን ሰሎሞንን) ትታ ሌላ ፍቅረኛ (የበግ እረኛ) ስታሳድድ ያየት የመጀመሪያው ባሏ እንዴት በፍቅር አሸንፎ ወደ ቤተ መንግሥቱ እንዳመጣት ነው ከሚለውም ጋር የሚቃረን ነው:: መጽሐፈ ማሕልይ የፍቅር መጽሐፍ ነው:: የፍቅርን ውበት፣ ኀይል፣ ግለትና ታላቅነት ልዩ በሆነ መንገድ የሚገልጽ መጽሐፍ ነው:: አንድ ሰው በራሱ ሕይ ወት ውስጥ ፍቅርን በመለያየትና በመዋደድ፣ በሥቃይና በደስታ፣ በውጥ ረትና በእርካታ ውስጥ እንዴት እንዳየው በተመክሮ የሚናገር መጽሐፍ ነው:: መጽሐፉ በሌሎች ሕ ዝቦች ባሕል ውስጥ ስለ ፍቅር ከሚነገረው ነገር ጋር ብዙ የሚጋራው ነገር አለ፤ መሠረት ያደረገውም ከሥነ ፍጥረት ላይ የወሰዳቸውን ምስል ከሣች ዘይቤዎችን ነው::

### መሪ ሐሳቡና ትምህርተ መለኮቱ

በጥንቷ እስራኤል ማንኛውም ነገር በቃል ነው የሚገለጸው:: ለምሳሌ ሰዎች አክብሮታቸውን፣ ምስጋናቸውን፣ ቍጣቸውን፣ ሐዘናቸውን፣ ሥቃያቸውን፣ እምነታቸውን፣ ወዳጅነታቸውን፣ ታዛዥነታ ቸውን፣ ታማኝነታቸውን፣ ተስፋቸውን፣ ጥበባቸውን፣ ጭካኔያቸውን፣ ኑዛዜያቸውን ሁሉ የሚያስታው ቁት በቃላት ነው:: በዚህ መጽሐፍ ውስጥ በቃላት ተነግሮ የምናገኘው ደግሞ ስለ "ፍቅር" ነው፤ ፍቅር የእግዚአብሔር ምርጥ ስጦታ እንደ ሆነ፣ ውብና ብርቱ በሆኑ ቃላት ተገልጾአል:: በምሳሌ 8፥1-9፥12

ላይ ጥበብ በሴት ድምፅ እንደ ተገለጸች ሁሉ፣ በዚህም መጽሐፍ ውስጥ ስለ ፍቅር የተነገረው በሴት ድምፅ ነው። ይህም ፍቅርና ጥበብ እንደ ሴት ወንዶችን የመማረክና የመሳብ ኀይል እንዳላቸው ያሳያል።

ይህች ድምፀ ሴት ስለ ፍቅር የምትናገረው በጥልቀት ነው። የፍቅርን ውበትና ደስታ ምስል ከሣች በሆኑ ቃላት ትስልልናለች። ፍቅር ልዩና የእርሷ ብቻ እንደ ሆነች ("ውዴ የእኔ ነው፤ እኔም የእርሱ ነኝ" 2፥16) እንዲሁም በራሷ የምትነሣሣና የምትቀሰቀስ ("ፍቅርን እንዳታስነሡት ወይም እንዳትቀሰቅሱት" 2፥7 ) እንደ ሆነች በግልጽ ትናገራለች። ከዚህ በተጨማሪ ፍቅር ብርቱ ኀይል እንዳላት ታውጃለች። ፍቅር አስፈሪውን ጠላት ይኸውም ሞትን እንኳ ድል ትነሣለች፤ እንደ እሳት ወላፈን ትጋረፋለች፤ የውሃ ብዛት እንኳ ሊያበርዳት አይችልም (8፥6-7)። የፍቅርን ውድነትና ክቡርነትም ትገልጽልናለች፤ ፍቅርን ሊገዛ የሚችል ሀብት ከቶ የለም (8፥7)። በግልጽ ሳይሆን በስውር የእግዚአብሔር ስጦታ እንደ ሆነችም ትጠቁመናለች።

## ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ

ማሕልየ መሓልይን በጥሞና የሚያነብ ማንኛውም ሰው የባለ ቅኔውን የአጻጻፍ ችሎታ ሳያደንቅ አያልፍም። ግርድፍ የሆነውን አነጋገር እየተወ ስሜትን ፈንቅሎ ወደሚያዘልለው አገላለጽ ሲያመራ ተደራሲያኑ ቁጭ ብድግ ማለት ይጀምራሉ። የተደራስያኑን ስሜት ፍጹም ሊቈጣጠር የቻለው ተለዋጭ ዘይቤዎችን፣ ምስል ከሣች አባባሎች፣ ከሥነ ፍጥረት የተዋሳቸውን አነጋገሮች በመጠቀም ነው። "ውዴ" እያለ የሚጠራትን ሴት ፍቅር ሚዳቋ ከምትውልበት ስፍራ እያመሳሰለ ሲገልጽ፣ "በውብ አበቦች መካከል" ያለሽ (2፥16)፣ ስለ ጡቶቿ ሲናገር "መንታ ሆነው የተወለዱ ... ሁለት የሚዳቋ ግልገሎችን ይመስላሉ" (4፥5)፣ ስለ ማራኪነቷ ሲያወሳ ደግሞ ምርጥ በሆኑ ፍሬዎች የተሞላሽ ነሽ (4፥12-16) ይላል። እነዚህ ሁሉ ጸሓፊው ስሜት እንዲጨብጡና እንዲያነሣሡ የተጠቀመባቸው የአገላለጽ ስል ቶች ናቸው።

መጽሐፉ ንዑሳን ርእሶቹን የሚያያይዝ አንድ ወጥ ታሪክ አለው ወይ የሚለው ጥያቄ እስከ አሁን ድረስ መልስ አላገኘም። ይሁንና በፍቅር ጨዋታው ውስጥ የተያያዙ ትዕይንቶች እንዳሉ ግልጽ ነው ("አስተዋፅኦ" የሚለውን ይመ)።

ብዙዎች እንደሚስማሙት ከሆነ፣ የማሕልየ ገለጻ ከሮ የሚገኘው በ8፥6-7 ላይ ነው። በዚህ ክፍል ውስጥ ፍቅር ብርቱና ፋይዳውም/ዋጋውም አቻ የሌለው እንደ ሆነ በሚገባ ተጠቅሶአል። ከዚህ በኋላ ጽሑፉ ረጋና ዘና ብሎ ወደ መደምደሚያው ያመራል። በሁለት ፍቅረኛሞች መካከል ሊኖረው ስለሚገባ የእርስ በርስ ፍቅር ከተናገረ በኋላ ፍቅር ነዋሪ እንደ ሆነ ያሳስባል። ይህ የመጨረሻው ክፍል (8፥8-14) በመግቢያው ላይ ወደ ተወሳው ሐሳብ በመመለስ ስለ አትክልቱ ቦታና ስለ ሰሎሞን (ንጉሡ) በመናገር ሁለቱን ክፍሎች (ማለትም 8፥8-12ን ከ1፥2-6) ጋር ያስተሳስራቸዋል።

በዚህ የፍቅር ማሕልይ ውስጥ ጐልቶ የሚታየው "ውዴ" የተባለችው ሴት ድምፅ ነው። የእርሷ የፍቅር ልምድ ነው በመጽሐፉ ውስጥ ደምቆ የሚታየው። ምክንያቱም ስትወድም ሆነ ስትወደድ የምትታየው እርሷ ናት። መጽሐፉ የሚጀምረው ወዳጇ እንዲስማት በመመኘትና ወዳጇ ከእርሷ ጋር እንዲጣበቅ በመጋበዝ ነው።

## አስተዋፅኦ

1. ርእስ (1፥1)
2. *የመጀመሪያው ግንኙነት* (1፥2-2፥7)
3. *ሁለተኛው ግንኙነት* (2፥8-3፥5)
4. *ሦስተኛው ግንኙነት* (3፥6-5፥1)
5. *አራተኛው ግንኙነት* (5፥2-6፥3)
6. *አምስተኛው ግንኙነት* (6፥4-8፥4)
7. *የጽሑፉ የመጨረሻው ደረጃ ላይ ደርሶ መክረር* (8፥5-7)
8. *መደምደሚያ* (8፥8-14)

**1** ከመዝሙር ሁሉ የሚበልጥ የሰሎሞን መዝሙር።

**ሙሽራዪቱ**

[2]በከንፈሩ መሳም ይሳመኝ
ፍቅርህ ከወይን ጠጅ ይልቅ ደስ
ያሰኛልና።
[3]የሽቱህ መዐዛ ደስ ያሰኛል፤
ስምህ እንደሚፈስ ሽቱ ነው፤
ታዲያ ቈነጃጅት ቢወዱህ ምን
ያስደንቃል
[4]ይዘኸኝ ሂድ፤ እንፍጠን፤
ንጉሡ ወደ ዕልፍኞቹ አምጥቶኛል።

**ባልንጀሮቿ**

በአንተ[u] ደስ ይለኛል፤ ሐሤትም
እናደርጋለን፤
ከወይን ጠጅ ይልቅ ፍቅርህን
እንወድሳለን።

**ሙሽራዪቱ**

አንተን እንደዚህ ማፍቀራቸው
ትክክል ነው።
[5]እናንት የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት ሆይ፤
እኔ ጥቍር ነኝ፤ ይሁን እንጂ
ውብ ነኝ፤
ጥቍረቴ እንደ ቄዳር ድንኳኖች፣
እንደ ሰሎሞን[^] ቤተ መንግሥት
መጋረጃዎችም ነው።
[6]ጥቍር ስለ ሆንሁ ትኵር
ብላችሁ አትዩኝ፤
መልኬን ያጠቈረው ፀሓይ ነውና፤
የእናቴ ልጆች ወንድሞቼ ተቈጡኝ፤
የወይን ተክል ቦታዎችም
ጠባቂ አደረጉኝ፤
የራሴን የወይን ተክል ቦታ ተውሁት።
[7]ውዴ ሆይ፤ መንጋህን የት
እንደምታሰማራ፣
በቀትርም የት እንደምትመስጋቸው
እባክህ ንገረኝ፤
በወዳጆችህ መንጎች ኋላ፣
ፊቷን ሸፍና እንደምትቅበዘበዝ
ሴት ለምን ልሁን?

**ባልንጀሮቿ**

[8]አንቺ ከሴቶች ሁሉ ይበልጥ የተዋብሽ
ሆይ፤ የማታውቂ ከሆነ፣
የበጎቹን ዱካ ተከተዪ፤
የፍየል ግልገሎችሽንም፣
በእረኞቹ ድንኳን አጠገብ አሳማሪ።

**ሙሽራው**

[9]ውዴ ሆይ፤ የፈርዖንን ሠረገሎች ከሚስቡ
ፈረሶች መካከል፣
በአንዲቱ ባዝራ መሰልሁሽ።
[10]ጕንጮችሽ በጕትቻ፣
ዐንገትሽም በዕንቍ ሐብል አጊጠዋል።
[11]እኛም ባለ ብር ፈርጥ፣
የወርቅ ጕትቻ እናሠራልሻለን።

**ሙሽራዪቱ**

[12]ንጉሡ ማእዱ ላይ ሳለ፣
ሽቱዬ መዐዛውን ናኘው።

1፥1 1ነገ4፣32፤ መዝ45 ርዕስ
1፥2 ቍ4፤ ዘፍ 14፥18፤ መሳ9፥13፤ማሕ 4፥10፤8፥6
1፥3 አስ2፥12፤ መዝ45፥8፡14፤ መክ7፥1
1፥4 ቍ2፤ መዝ45፥15፤ ማሕ2፥3
1፥5 ዘፍ25፥13፤ ማሕ2፥14፤4፥3፤ 5፥16
1፥6 ማሕ2፥15፤ 7፥12፤8፥12
1፥7 ዘፍ24፥65፤ ኢሳ13፥20
1፥8 ማሕ5፥9፤6፥1
1፥9 2ዜና1፥17
1፥10 ማሕ5፥13፤ ኢሳ61፥10
1፥12 ማሕ4፥11-14

[u]4 በዕብራይስጥ ነጠላ ተባዕታይ ነው።
[^]5 ወይም ሳልማ

1፥1 *ከመዝሙር ሁሉ የሚበልጥ፤* ከመዝሙር ሁሉ ተወዳጅነት ያለው መዝሙር ነው (በመግቢያው ላይ ርእስ የሚለውን ይመ)። ሰሎሞን አንድ ሺህ አምስት መዝሙሮች እንደ ጻፈ በ1ነገ 4፥32 ላይ ተገልጾአል። *የሰሎሞን፤* በመግቢያው ላይ ርእስ፣ ጸሓፊውና የተጻፈበት ጊዜ የሚለውን ይመ።

1፥2-3 *መሳም... ፍቅርህ...ሽቱህ፤* በ4፥10-11 ላይ፣ "ፍቅርሽ...የሽቱሽም... ከንፈሮችሽ" ተብሉ ከተጠቀሰው ጋር ያነጻጽሩ።

1፥2 *ፍቅርህ፤* በመዳሰስ፣ በማቀፍና በጋብቻ በመጣመር ይገለጻል (ቍ 4፤ 4፥10፤ 7፥12፤ ምሳ 7፥18፤ ሕዝ 16፥8፤ 23፥17 ይመ)። *ከወይን ጠጅ ይልቅ ደስ ያሰኛል፤* ቍ 4 ይመ። በ4፥10 ላይ ሙሽራው ተመሳሳይ በሆነ መንገድ ስለ ሙሽራዪቱ ፍቅር ይናገራል።

1፥3 *የሽቱህ፤* ጣፋጭ ሽታ ካለው ቅመምና ከርቤ በዘይት ተደባልቆ የተሠራ ነው። *ስምህ፤* የሙሽራው ስም ሲጠራ መልካም መዐዛ እንዳለው ሽቱ አየሩን ሁሉ ያውዳል። "ስም" እና "ሽቱ" በዕብራይስጡ ትርጕም ተመሳሳይ ድምፀት አላቸው። *ቈነጃጅት፤* በቤተ መንግሥት ያሉትን ልጃገረዶች ያመለክት ይሆናል (6፥8-9 ይመ)።

1፥4 *ንጉሡ፤* ሰሎሞንን ሊያመለክት ይችላል። *ዕልፍኞቹ፤* ለንጉሡ የተለዩ ክፍሎች ናቸው። *ከወይን ጠጅ ይልቅ ፍቅርህን እንወድሳለን፤* እንደዚህ ያስኘው በቍ 2 ላይ የተጠቀሰው ምክንያት ነው።

1፥5 *የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፤* በቍ 3 ላይ "ቈነጃጅት"ን በመጽሐፉ ውስጥ ደግሞ ንኡስ ርእስ ሆኖ በተደጋጋሚ የተጠቀሰውን "ባልንጀሮቿ"ን ሳያመለክት አይቀርም። *ጥቍር፤* ፀሓይ እጅግ ስላጠቈራት (ቍ 6 ይመ)፣ መልኳ የሚስብ ሆኖ አልተገኘም። *ቄዳር፤* የኢሳ 21፥16ማብ ይመ። *ድንኳኖች... መጋረጃዎችም፤* ከጥቍር ፍየል ጠጕር በእጅ ተፈትለው የተሠሩ ናቸው።

1፥6 *የራሴን የወይን ተክል ቦታ፤* በ8፥12 ላይ እንደ ተጠቀሰው ምናልባት የራሷዋን ሰውነት ያመለክታል (2፥15 ይመ)። የወይን ተክል ቦታ የወይን ጠጅ የሚያገኝበት ስለ ሆነ፣ ለዚህ ክፍል የሚስማማ ተለዋጭ ዘይቤ ነው። ከፍቅር የሚገኘውም ደስታ ከወይን ጠጅ ከሚገኘው ደስታ ጋር ተነጻጽሮአል (የቍ 2 ማብ ይመ)። ሙሽራዪቱም ጣፋጭ ፍሬ ለሙሽራው ከሚሰጥ የአትክልት ቦታ ጋር ተነጻጽራለች (የ4፥12 ማብ ይመ)።

1፥7 *ውዴ ሆይ፤* 3፥1ይመ። *መንጋህን የት እንደምታሰማራ፤* እዚህ ላይ ሙሽራው እንደ እረኛ ተገልጾአል፤ በቍ 8 ላይ ደግሞ ሙሽራይቱ እንደ እረኛ ተገልጻለች። *በቀትርም፤* አየሩ ሞቃት ሲሆን የዕረፍት ጊዜ ነው። *ፊቷን ሸፍና ... ሴት፤* እንደ ሴትኛ ዐዳሪ ማለት ነው (ዘፍ 38፥14-15 ይመ)። ሙሽራዪቱ ሴተኛ አዳሪ መስላ ሙሽራውን በእረኞች መካከል ልትፈልግ አትሄድም።

1፥8 *የተዋብሽ፤* ሙሽራዪቱን ያመለክታል፤ ቃሉ በቍ 15፤ 2፥10፡13፤ 4፥1፡7፤ 5፥9፤ 6፥1፡4፡10 ላይም ተጠቅሶአል። *የፍየል ግልገሎችሽንም፤* ሙሽራዪቱ እንደ እረኛ ተገልጻለች (ቍ 7ይመ)። *በእረኞቹ ድንኳን፤* ሙሽራዪቱ ከእረኞቹ ጋር ግንባር በመፍጠር ሙሽራው የት እንዳለ ለማወቅ ቻለች።

1፥9 *ውዴ ሆይ፤* ለሙሽራዪቱን ብቻ የተሰጠ መጠሪያ ነው (የቍ 13 ማብ ይመ)። ሙሽራዪቱን ለማቈላመጥ ይህን ቃል ተጠቅሞአል። *የፈርዖንን ሠረገሎች ከሚስቡ ... መካከል በአንዲቱ፤* የግብፅን ሠረገላ በሚጐትቱት ድንጕላ ፈረሶች መካከል እንዳለች ባዝራ ውበቷዋ ማራኪ ነው። ሰሎሞን ፈረሶችን ከግብፅ ያስመጣ እንደ ነበር በ1ነገ 10፥28 ላይ ተጠቅሶአል።

1፥11 *እኛም፤* የኢየሩሳሌምን ቈነጃጅት ሳያመለክት አይቀርም።

1፥12 *ማእዱ ላይ ሳለ፤* ንጉሡ በድንክ ዐልጋው ላይ ደገፍ ብሉ በማእድ መቀመጡን ያሳያል። *ሽቱዬ፤* በህንድ አገር ከሚበቅልና ዓመቱን ሁሉ ከሚቈይ ተክል ሥር የሚጨመቅ ጥሩ መዐዛ ያለው የናርዶስ ሽቱ ነው (4፥13-14፤ ማር 14፥3፤ ዮሐ12፥3 ይመ)።

[13]ውዴ ለእኔ በጡቶቼ መካከል እንዳረፈ፣
በምቋጠሪያ እንዳለ ከርቤ ነው።
[14]ውዴ ለእኔ ከዓይንጋዲ የወይን ተክል
ቦታ፣
እንደ መጣ የሄና አበባ ዕቅፍ ነው።

**ሙሽራው**

[15]ውዴ ሆይ፤ እንዴት ውብ ነሽ
እንዴትስ ያለሽ ቈንጆ ነሽ
ዐይኖችሽም እንደ ርግብ
ዐይኖች ናቸው።

**ሙሽራዪቱ**

[16]አንተ ውዴ ሆይ፤ እንዴት ውብ ነህ
እንዴትስ ታምራለህ
ዐልጋችንም እንደ ለምለም ሣር ነው።

**ሙሽራው**

[17]የቤታችን ተሸካሚዎች ዝግባዎች፣
የጣራችን ማዋቀሪያዎችም ጥዶች
ናቸው።

**ሙሽራይቱ**

# 2

እኔ የሳሮን ጽጌረዳ፣
የሸለቆም አበባ[*] ነኝ።

**ሙሽራው**

[2]በእሾኽ መካከል እንዳለ ውብ አበባ፣
ውዴም በቈነጃጅት መካከል እንዲሁ
ናት።

**ሙሽራዪቱ**

[3]በዱር ዛፎች መካከል እንዳለ እንኰይ፣
ውዴም በጕልማሶች መካከል እንዲሁ
ነው፤
በጥላው ሥር መቀመጥ ደስ ያሰኛል፤
የፍሬውም ጣፋጭነት ያረካኛል።
[4]ወደ ግብዣው አዳራሽ ወሰደኝ፤
በእኔ ላይ ያለው ዐላማው
ፍቅር ነው።
[5]በዘቢብ አበረታቱኝ፤
በእንኰይም አስደስቱኝ፤
በፍቅሩ ተይዤ ታምሜአለሁና።
[6]ግራ እጁን ተንተርሻለሁ፤
ቀኝ እጁም ዐቅፎኛል።
[7]እናንት የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፣
ራሱ እስኪፈልግ ድረስ፣
ፍቅርን እንዳታስነሡት ወይም
እንዳትቀሰቅሱት፣
በሚዳቋና በሜዳ ዋልያ አማጥናችኋለሁ።
[8]እነሆ፤ የውዴ ድምፅ
በተራሮች ላይ እየዘለለ፣
በኰረብቶችም ላይ እየተወረወረ፣
ሲመጣ ይሰማኛል።
[9]ውዴ ሚዳቋ ወይም የዋልያ ግልገል
ይመስላል፤
እነሆ፤ ከቤታችን ግድግዳ ኋላ ቆሞአል፤
በመስኮት ትክ ብሎ ወደ ውስጥ ያያል፤
በፍርግርጉም እያሾለከ ይመለከታል።
[10]ውዴም እንዲህ አለኝ፤
"ፍቅሬ ሆይ፤ ተነሺ፤
አንቺ የእኔ ቈንጆ፤ ከእኔ ጋር ነዪ።
[11]እነሆ! ክረምቱ ዐለፈ፤
ዝናሙም አባርቶ አበቃ፤
[12]አበቦች በምድር ላይ ታዩ፤
የዝማሬ ወቅት ወጥቶአል፤
የርግቦች ድምፅም፣
በምድራችን ተሰማ።
[13]በለስ ፍሬዋን አፈራች፤
ያበቡ ወይኖችም መዐዛቸውን ሰጡ፤
ፍቅሬ ሆይ፤ ተነሺና ነዪ፤
አንቺ የእኔ ቈንጆ፤ ከእኔ ጋር ነዪ።"

1፥13 ዘፍ37፥25
1፥14 ቍ16፤ 1ሳሙ23፥29፤ 2ዜና20፥2፤ማሕ 2፥3፡17፤4፥13፤5፥8
1፥15 መዝ74፥19፤ ማሕ2፥14፤ 4፥1፡7፤5፥2፡12፤6፥9፤7፥6፤ ኤር48፥28
1፥16 ቍ14
1፥17 1ነገ 6፥9
2፥1 1ዜና27፥29፤ ማሕ5፥13፤ ኢሳ35፥1፤ሆሴ14፥5
2፥3 ማሕ1፥4፡14፤4፥16
2፥4 ዘኍ1፥52፤ አስ1፥11
2፥5 ማሕ5፥8፤7፥8
2፥6 ምሕ8፥3
2፥7 ማሕ3፥5፤ 5፥8፤8፥4
2፥8 ቍ17፤ማሕ 8፥14
2፥9 ቍ17፤ 2ሳሙ2፥18፤ማሕ8፥14
2፥13 ማሕ7፥12፤ ኢሳ28፥4፤ኤር24፥2፤ ሆሴ9፥10፤ሚክ7፥1፤ ናሆ3፥12

*1 ጸደይ ከመሆኑ ቀደም ብሎ የሚቀበል ቢጫ፣ሐምራዊና ነጭ ቀለም ያሉት የአበባ ተክል ዝርያ ሊሆን ይችላል፡

1፥13 *ውዴ፤* ሙሽራውን የሚያለክት ነው (የቍ 9 ማብ ይመ)። *ከርቤ፤* በዓረብ አገር በኢትዮጵያና በሕንድ ከሚበቅል የበለሳን ዛፍ ቅርፊት የሚወጣ መልካም መዐዛ ያለው ሙጫ ነው፤ ማራኪ ስለ ሆነ ሽቱውን ሴቶች ይወዱታል (አስ 2፥12፤ ምሳ 7፥17)። ለንጉሣዊ ቤተ ሰብ የሰርግ ልብሶችም ይጠቀሙበት ነበር (መዝ 45፥8)፤ ሰብአ ሰገልም ለንጉሥ የሚገባ ስጦታ አድርገው (ማቴ 2፥2፡11)፣ ኢየሱስ ሲወለድ ያቀረቡት ይህንኑ ከርቤ ነበር፤ የተቀደሰ መቀቢያ ዘይት ሲቀመም ከሚጨመሩት ንጥረ ቅመሞች አንዱ ከርቤ ነበር (ዘፀ 30፥23)።

1፥14 *ከዓይንጋዲ፤* በሙት ባሕር ምዕራባዊ ጠርዝ ላይ የሚገኝ የምንጭ ውሃ የሚያጠጣው የምድረ በዳ ለምለም ስፍራ ነው፤ ዳዊት ከሳኦል ለመሰወር በዚህ ሥፍራ ተሸሸገ (1ሳሙ 24፥1)። *የሄና፤* ችፍግ ብሎ የተያያዘ አበባና መልካም ሽታ ያለው፣ በመካከለኛው ምሥራቅ ምናልባትም በቆጵሮስ የሚበቅል ነው።

1፥15 *ውዴ ሆይ፤ እንዴት ውብ ነሽ፤* 4፥1፤ 6፥4 ይመ፤ ከቍ 16 ጋር ያነጻጽሩ። ውዴ ሆይ፤ የቍ9 ማብ ይመ። *ርግብ፤* 4፥1 ይመ።

1፥16 *ውብ ነህ፤* የቍ 8 ማብ ይመ። *ለምለም ሣር፤* ሙሽራውና ሙሽራዪቱ በዛፎች ሥር ባለው ሜዳ ላይ ጋደም ይላሉ።

2፥1 *ጽጌረዳ፤* ኢሳ 35፥1-2 ይመ። *የሳሮን፤* ከቀርሜሎስ ተራራ በስተ ደቡብ በባሕር ጠረፍ የምትገኝ ለምለም ሜዳ ናት

2፥2 *ውዴም፤* የ1፥9 ማብ። *በቈነጃጅት፤* 1፥3 ማብ ይመ።

2፥4 *ዐላማው፤* 6፥4፤ ዘኍ 2፥2፤ መዝ 20፥5 ይመ። ንጉሡ ለሙሽራዪቱ ያለው ፍቅር እንደ ትልቅ ወታደራዊ ሰንደቅ ዐላማ ለማንም እንዲታይ ተደርጎአል።

2፥5 *በዘቢብ ... በእንኰይም፤* ፍቅርን ለመግለጽ የሚደረገውን መተሻሸትና ማቀፍ የሚያመለክት ተለዋጭ ዘይቤ ሊሆን ይችላል።

2፥7 በማሕልዩ ውስጥ እንደ አዝማች ብዙ ጊዜ የተደጋገመ ሐሳብ ነው (3፥5፤8፥4 ይመ፤ ከ5፥8 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህን ዘወትር የምትናገረው ሙሽራዪቱ ስትሆን፣ የምትናገረውም ከወዳጇ ጋር ካላት አካላዊ ግንኙነት አንጻር ነው። *የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፤* የ1፥5 ማብ ይመ። *አማጥናችኋለሁ፤* አምላችኋለሁ ማለት ነው። *በሚዳቋና ... ዋልያ፤* በምናባዊ የፍቅር አገላለጽ፤ ዋልያና ሚዳቋ ለመሐላው እንደ ምስክር ተቈጥረው ሊሆን ይችላል። ይህም፣ ጸሐፊው ስለ ተፈጥሮ ደጋግሞ ከሚጠቅሰው ሐሳብ ጋር የሚስማማ ነው። *ራሱ እስኪፈልግ ድረስ፤* ከልብ ባልሆነ መንገድ ወይም በማስመሰል ፍቅርን ማነሣሣት ተገቢ እንዳልሆነ የሚያስገነዝብ በሳል ምክር ሙሽራዪቱ ካላት የፍቅር ልምድ ይገኛል።

2፥9 *ሚዳቋ፤* በሰውነት ቅርጹና በውበት የሚደነቅ እንስሳ ነው። *የዋልያ ግልገል፤* የወጣትነት ጥንካሬን የሚገልጽ ተስማሚ ተነጻጻሪ ዘይቤ ነው (ከኢሳ 35፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። *ትክ ብሎ ... ያያል፤ ... በፍርግርጉም፤* በመጓጓት ላይ ያለው ወዳጇ ሙሽራዪቱ ከእርሱ ጋር ለመገናኘት ራሷ ስታዘጋጅ ሊመለከታት ጥረት ያደርጋል።

2፥10 *ተነሺ ... ከእኔ ጋር፤* ቍ 13 ይመ፤ ከ7፥11-13 ጋር ያነጻጽሩ። *የእኔ ቈንጆ፤* የ1፥8 ማብ ይመ።

*2፥11-13፤* ለጸደይ ወራት መግባት የመጀመሪያ ምልክት ነው (6፥11፤7፥12 ይመ)፤ ይህም ፍቅረኞች ፍቅራቸውን የሚገልጹበት ጊዜ ነው።

ሙሽራው

[14]አንቺ በገደል ዐለት ንቃቃት፣
በተራሮችም ባሉ መደበቂያ ስፍራዎች
ውስጥ ያለሽ ርግቤ ሆይ!
ፊትሽን አሳይኝ፤
ድምፅሽንም አሰሚኝ፤
ድምፅሽ ጣፋጭ፣
መልክሽም ውብ ነውና።
[15]የወይን ተክሉን ቦታ፣
በማበብ ላይ ያለውን የወይን ተክል
ቦታችንን፣
የሚያጠፉትን ቀበሮዎች፣
እነዚያን ትንንሽ ቀበሮዎች አጥምዳችሁ
ያዙልን።

ሙሽራዪቱ

[16]ውዴ የእኔ ነው፤ እኔም የእርሱ ነኝ፣
እርሱ መንጋውን በውብ አበቦች መካከል
ያሰማራል።
[17]ጎሕ ከመቅደዱ በፊት፣
ጥላውም ሳይሸሽ፣
ውዴ ሆይ፤ ተመለስ፣
ሚዳቋን ምሰል፤
ወይም በወጣ ገባ ኰረብቶችˉ
እንዳለው የዋልያ ግልገል ሁን።

**3** ሌሊቱን ሙሉ በአልጋዬ ላይ ሆኜ፣
ውዴን ተመኘሁ፤
ተመኘሁት፤ ነገር ግን አላገኘሁትም።
[2]ተነሥቼ ወደ ከተማዪቱ እወጣለሁ፤
በዋና ዋና መንገዶችና በአደባባዮች
እዘዋወራለሁ፤
ውዴንም እፈልገዋለሁ፤
ስለዚህም ፈለግሁት፤ ነገር ግን
አላገኘሁትም።
[3]በከተማዪቱ ውስጥ ሲዘዋወሩ፣
የከተማዪቱ ጠባቂዎች አገኙኝ፤
እኔም፣ "ውዴን አይታችኋል?"
አልኋቸው።

2፥14 ዘፍ8፥8፤ ማሕ1፥5፡15
2፥15 መሳ15፥4፤ ማሕ1፥6፤7፥12
2፥16 ማሕ4፥5፤ 6፥3፤7፥10
2፥17 ቍ8፡9፤ ማሕ1፥4፤4፥6
3፥1 ማሕ5፥6
3፥3 ማሕ5፥7
3፥4 ማሕ6፥9፤ 8፥2፡5
3፥5 ማሕ2፥7፤8፥4
3፥6 ዘፀ30፥34፤ ማሕ4፥6፡14፤8፥5
3፥7 1ሳሙ8፥11
3፥8 ኢዩ15፥22፤ መዝ91፥5
3፥11 ኢሳ3፥16፤ 4፥4፤32፥9-13፤ 54፥5፤62፥5፤ ኤር3፥14

[4]ከእነርሱ ጥቂት ዕልፍ እንዳልሁ፣
ውዴን አገኘሁት፤
ያዝሁት፤
ወደ እናቴ ቤት እስካመጣው፣
በማሕፀን ወደ ተሸከመችኝም ዕልፍኝ
እስካገባው ድረስ አልለቀውም።
[5]እናንት የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፤
ራሱ እስኪፈልግ ድረስ፣
ፍቅርን እንዳታስነሡት ወይም
እንዳትቀሰቅሱት፣
በሚዳቋና በሜዳ ዋልያ አማጥናችኋለሁ።
[6]ከከርቤና ከዕጣን፣
ከነጋዴም ቅመማ ቅመም ሁሉ በተዘጋጀ
ሽቱ፣
መዐዛዋ የሚያውድ፣
እንደ ጢስ ዐምድ ከምድረ በዳ የም
ትወጣው ይህች ማን ናት?
[7]እነሆ፤ የሰሎሞን ሠረገላ
በታዋቂዎቹ የእስራኤል መኳንንት፣
ሥልሳ ጦረኞች ታጅባለች፤
[8]ሁሉም ሰይፍ የታጠቁ፣
ሁሉም በጦርነት የተፈተኑ ናቸው፤
የሌሊት አደጋን ለመከላከልም፣
እያንዳንዳቸው ሰይፋቸውን በወገባቸው
ታጥቀዋል።
[9]ንጉሥ ሰሎሞን የራሱን ሠረገላ ሠራ፤
የሠራውም ከሊባኖስ በመጣ ዕንጨት
ነው።
[10]ምሰሶዎቹን ከብር፣
መደገፊያውንም ከወርቅ ሠራ፤
መቀመጫውም በሐምራዊ ሐር የተሸፈነ
ነው፤
ውስጡም በኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፣
አምሮ የተለበጠ ነው።ˉ
[11]እናንት የጽዮን ቈነጃጅት ውጡ፤
ንጉሥ ሰሎሞን አክሊሉን ደፍቶ እዩት፤

ˉ17 *ወይም የቤጠር ኰረብቶች*
ˉ10 *ወይም የተለበጠውም ውስጥ፣ ከኢየሩሳሌም ቈነጃጅት የሆነ የፍቅር ስጦታ*

2፥14 *በተራሮችም ባሉ ... ርግቤ፤* ከመዝ 55፥6-8፤ ከኤር 48፥28 ጋር ያነጻጽሩ።

2፥15፤ ይህን የተናገረችው ሙሽራዪቱ ልትሆን ትችላለች። *የወይን ተክሉን ቦታ፤* "የራሴንም የወይን ተክል ቦታ" ተብሎ በ1፥6 ላይ እንደ ተጠቀሰው የሙሽራውን አካላዊ ውበት የሚያመለክት ተለዋጭ ዘይቤ ሳይሆን አይቀርም። ይህ ክፍል ፍቅረኞቹ በመካከላቸው ያለውን ወዳጅነት ከሚያበላሽ ከማናቸውም ነገር ሁሉ የተጠበቀ እንዲሆኑ ያሳስባል። *በማበብ ላይ ያለውን፤* ቍንጅናቸው እጅግ ማራኪ ሆኖ የሚታይበትን ጊዜ ያመለክታል።

2፥16 *ውዴ የእኔ ነው፤ እኔም የእርሱ ነኝ፤* 6፥3፤7፥10 ይመ። ማንም ጣልቃ ሊገባ በማይችልበት ሁኔታ እርስ በርሳቸው ተጣምረዋል። *በውብ አበቦች መካከል ያሰማራል፤* በዚህ ስፍራ ሙሽራው ከሚዳቋ ጋር ተነጻጽሮአል (ቍ 17 ይመ)። 'ማሰማራት'የሚለው ቃል ሙሽራው በሙሽራዪቱ ውበት ደስ መሰኘቱን የሚገልጽ ተለዋጭ ዘይቤ ነው (6፥2-3 ይመ)።

*3፥1፤* ይህ ጥቅስ በፍቅር ልምምድ ውስጥ አዲስ ምዕራፍ የሚጀምር ነው። *ሌሊቱን ሙሉ፤* በቀን ከሚያውክ ነገር ነጻ ስለሚሆን፣ የሰው አእምሮ በሌሊት የበለጀ ያስገባል።

3፥3 *ጠባቂዎች፤,* በከተማ በሮች (ነህ 3፥29፤ 11፥19፤ 13፥22 ይመ) እና በቅጥሮች ላይ (5፥7፤ 2ሳሙ 13፥34፤ 18፥24-27፤ 2ነገ 9፥17-20፤ መዝ 127፥1፤ ኢሳ 52፥8፤ 62፥6 ይመ) ዘብ ይቆሙ ነበር፤ በምሽትም እየተዘዋወሩ ጒዳናዎችን ይቃኙ ነበር (5፥7 ይመ)።

3፥4 *እናቴ፤* ማሕልዩ ስለ እናቶች ደጋግሞ የሚያወሳ ሲሆን፣ ስለ አባቶች ግን ምንም አይጠቅስም።

*3፥5፤* የ2፥7 ማብ ይመ። "ማማጠኑ" ፍቅረኞቹ እጅግ በተቀራረቡበት ጊዜ እንደ ገና ተጠቅሶአል።

*3፥6-11፤* በጓደኞቻቸው የተነገረ ሳይሆን አይቀርም (8፥5 ይመ)፤ከእነርሱ ከሆነ ወደ ከተማው ቀርበው ሳሉ የሙሽራውንና የሙሽራዪቱን የሰርግ ሥርዐት የሚገልጽ ሊሆን ይችላል።

*3፥6፤* ይህ ጥቅስ በግንኙነቱ ውስጥ አዲስ ምዕራፍ የሚጀምር ነው። *ከምድረ በዳ ... ማን ናት?፤* ስለ ሙሽራዪቱ የሚናገረውን 8፥5 ይመ። *ከምድረ በዳ፤* የማይታረስና ወቅቱን ጠብቆ የሚበቅል ሣር ያለበት ደረቅ ምድር ነው። *ጢስ፤* የዕጣን ጢስ ነው (የዘፀ 30፥34 ማብ ይመ)። *ከነጋዴም፤* ከውጭ አገር መምጣቱን ያመለክታል።

3፥7 *ሠረገላ፤* ንጉሥና ንጉሣዊ ቤተ ሰብ በሰዎች ተሸካሚነት ከቦታ ቦታ ለመሄድ የሚጠቀሙበት፣ በከፍተኛ ደረጃ ያጌጠ፣ ወሰካ ነው (ቍ 910 ይመ)።

3፥8 *የሌሊት አደጋን፤* መዝ 91፥5 ይመ።

3፥10 *ምሰሶዎቹን፤* አጐበሩን ደግፈው የሚይዙ ናቸው። *ብር ... ወርቅ፤* ምናልባት ከሊባኖስ የመጣው ዕንጨት የተለበጠበት ይሆናል። *በሐምራዊ፤* የ7፥5፤ ዘፀ 25፥4 ማብ ይመ።

3፥11 *የጽዮን ቈነጃጅት፤* በሌላ ቦታ "የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት" ተብሎአል (የ1፥5ማብ ይመ)። *አክሊሉን፤* በጋብቻ ጊዜ

ዘውዱም ልቡ ሐሤት ባደረገባት፣
በዚያች በሰርጉ ዕለት፣
እናቱ የደፋችለት ነው።

**ሙሽራው**

**4** ውዴ ሆይ፤ እንዴት ውብ ነሽ!
እንዴትስ ያለሽ ቈንጆ ነሽ
ከመሸፈኛሽ ውስጥ ያሉት ዐይኖችሽ
እንደ ርግብ ዐይኖች ናቸው፤
ጠጕርሽም ከገለዓድ ተራራ
እንደሚወርድ፣
የፍየል መንጋ ነው።
[2]ጥርሶችሽ ወዲያው ተሸልተው፣
ከመታጠቢያ እንደ ወጡ የበግ መንጋ
ናቸው፤
ሁሉም መንታ መንታ የወለዱ፣
ከመካከላቸውም መካን የሌለባቸው
ናቸው።
[3]ከንፈሮችሽ ቀይ የሐር ፈትል ይመስላሉ፤
አፍሽም ውብ ነው፤
ከመሸፈኛሽ ውስጥ ያሉት ጕንጮችሽ፣
ለሁለት የተከፈለ ሮማን ይመስላሉ።
[4]ዐንገትሽ አምሮ የተሠራውን፣[ረ]
በላዩም የጦረኞች ጋሻዎች ሁሉ
ያሉበትን፣
ሺህ ጋሻዎች የተንጠለጠሉበትን፣
የዳዊትን የመጠበቂያ ማማ ይመስላል።
[5]ሁለቱ ጡቶችሽ መንታ ሆነው የተወለዱ፣
በውብ አበቦች መካከልም የተሰማሩ፣
ሁለት የሚዳቋ ግልገሎችን ይመስላሉ።
[6]ጎሕ ከመቅደዱ በፊት፣
ጥላውም ሳይሸሽ፣
ወደ ከርቤ ተራራ፣
ወደ ዕጣኑም ኰረብታ እወጣለሁ።
[7]ውዴ ሆይ፤ ሁለንተናሽ ውብ ነው፤
እንከንም አይወጣልሽም።
[8]ሙሽራዬ ሆይ፤ ከሊባኖስ አብረሽኝ ነዪ፤
አዎን ከሊባኖስ አብረሽኝ ነዪ፤
ከአንበሶች ዋሻ፣
ከነብሮች ተራራ፣
ከኤርሞን ራስ፣ ከሳኔር ጫፍ፣
ከአማና ዐናት ውረጂ።
[9]እኅቴ ሙሽራዬ፣ ልቤን ሰርቀሽዋል፤
በአንድ አፍታ እይታሽ፣
ከሐብልሽም በአንዱ ዕንቍ፣
ልቤን ሰርቀሽዋል።
[10]እኅቴ ሙሽራዬ፣ ፍቅርሽ እንዴት ደስ
ያሰኛል!
ፍቅርሽ ከወይን ጠጅ ይልቅ ምንኛ
የሚያረካ ነው፤
የሽቱሽም መዐዛ ከቅመም ሁሉ
ይልቅ የቱን ያህል ይበልጥ!
[11]ሙሽራዬ ሆይ፤ ከንፈሮችሽ የማር ወለላ
ያንጠባጥባሉ፤
ከአንደበትሽም ወተትና ማር
ይፈልቃል፤
የልብስሽም መዐዛ እንደ ሊባኖስ ሽታ
ነው።
[12]እኅቴ ሙሽራዬ፤ የታጠረ የአትክልት
ቦታ፣
ዙሪያውን የተከበበ ምንጭ፣ የታተመም
ፏፏቴ ነሽ።

[ረ]4 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም አይታወቅም

4፥1 ዘፍ24፥65፤ 37፥24፤ዘኍ32፥1፤ ማሕ1፥15፤6፥5፤ ኤር22፥6፤ሚክ7፥14
4፥2 ማሕ6፥6
4፥3 ማሕ1፥5፤ 5፥16፤6፥7
4፥4 መዝ144፥12፤ ሕዝ27፥10
4፥5 ምሳ5፥19፤ ማሕ2፥16፤7፥3
4፥6 ማሕ2፥17፤3፥6
4፥7 ማሕ1፥15፤5፥2
4፥8 ቍ9:12፤ ዘዳ3፥9፤1ዜና5፥23፤ ማሕ5፥1
4፥9 ቍ8፤ ዘፍ41፥42፤መዝ73፥6
4፥10 ቍ16፤ መሳ9፥13፤መዝ45፥8፤ ማሕ1፥2፤7፥6፤ ኢሳ57፥9
4፥11 መዝ19፥10፤ ማሕ5፥11 ሆሴ14፥6 144፥12 ቍ8:16፤ ምሳ5፥15-18፤ ማሕ5፥1፤6፥2፤ ኢሳ5፥7

የሚደረግ ጕንጕን አበባ ነው (ኢሳ 61፥10 ይመ)። *እናቱ፤* የቍ4 ማብ ይመ። እዚህ ላይ የሚናገረው ስለ ቤርሳቤህ ነው።

*4፥1-7፤* ስለ ሙሽራዪቱ ውበት የተሰጠውን ተጨማሪ አገላለጽ 6፥4-9፤7፥1-7 ላይ ይመ።

*4፥1-2፤* 6፥5-6 ይመ።

4፥1 *ውዴ ሆይ፤* እንዴት ውብ ነሽ፤ 1፥15 እና ማብ ይመ። *ከመሸፈኛሽ ውስጥ ያሉት ዐይኖችሽ፤* መላ ፊቷ ስለተ ሸፈነ፣ የሙሽራው ልብ ወደ ዐይኖቿ ላይ ነው። *ርግብ፤* 1፥15 እና ማብ ይመ። *የፍየል መንጋ፤* ብዙውን ጊዜ የከነዓን ፍየሎች ጥቋቍር እንደ ሆኑ ሁሉ (የ1፥5 ማብ ይመ)፣ የሙሽራው ጠጕ ርም ጥቍር ነው (5፥11)። *ከገለዓድ ተራራ እንደሚወርድ፤* ከራሷ ላይ ወደ ታች ዝንፍል ብሎ የወረደው የሙሽራዪቱ ረጅም ጥቍር ጠጕር ሙሽራው ከገለዓድ ተራሮች እጅብ ብለው የሚወርዱትን የጥቋቍር ፍየሎች መንጋ እንዲያስታወስ ያደርገ ዋል።

4፥2 *ወዲያው ተሸልተው፤* ንጹሕና ነጭ መሆናቸውን ያመለክታል። *ከመታጠቢያ እንደ ወጡ፤* ጥርሶቹ አሁንም ገና ርጥብ ናቸው።

4፥3 *ከንፈሮችሽ ቀይ፤* ሙሽራዪቱ እንደ ግብፅ ሴቶች ከንፈሯን ተቀብታ ይሆናል። *ከመሸፈኛሽ ውስጥ ያሉት ጕንጮ ችሽ፤* የቍ 1 ማብ ይመ። *ለሁለት የተከፈለ ሮማን፤* ክብና ቀይ መሆኑን ይገልጻል።

4፥4፤ ቀጥ ያለውና ያጌጠው የሙሽራዪቱ ዐንገት በጦረ ኞች ጋሻ እንዳሸበረቀው እንደ ከተማው ቅጥር ግንብ ነው (ከ7፥4 ጋር ያነጻጽሩ)።

4፥5፤ 7፥3ይመ። *የሚዳቋ ግልገሎች፤* እድገትን ሳይሆን ውበትንና ተስፋን የሚያመለክት ነው (ከ8፥8 ጋር ያነጻጽሩ)። *የሚዳቋ፤* የ2፥9 ማብ ይመ። ይህ ተነጻጻሪ ዘይቤ በሌላ ስፍራ ሙሽራውን ይገልጻል። *በውብ አበቦች መካከልም የተሰማሩ፤* ይህ ሐረግ የሚገልጸውን ሌላ ሐሳብ በ2፥16 እና ማብ ላይ ይመ።

4፥6 *ጥላውም ሳይሸሽ፤* 2፥17 ይመ። *ወደ ከርቤ ተራራ ... ወደ ዕጣኑም ኰረብታ፤* የሁለቱን ፍቅረኞች መቀራረብ የሚያ ሳዩ ተለዋጭ ዘይቤዎች ናቸው።

4፥8፤ ሙሽራዪቱ ወደ ሩቅ ተራራ የኰበለለችበት መስለው። *ከሊባኖስ ... ከኤርሞን ... ከአማና፤* በሰሜን በኩል የሚገኙ የተራራ ጫፎች ናቸው። *ከሳኔር፤* አሞራውያን የኤርሞ ንን ተራራ የሚጠሩበት ስም ነው (ዘዳ 3፥9)።

4፥9 *እኅቴ፤* በጥንት የቅርብ ምሥራቅ አገሮች የፍቅር ግጥም ሁለት ፍቅረኞች እርስ በርሳቸው “ወንድም” ወይም “እኅት” መባባላቸው የተለመደ ነበር (ቍ 10:12፤ 5፥1 ይመ)። *በአንድ አፍታ እይታሽ፤* 6፥5 እና ማብ ይመ።

4፥10 *ከወይን ጠጅ ይልቅ ... የሚያረካ፤* የ1፥2 ማብ ይመ። *የሽቱሽም መዐዛ*1፥3 ይመ። *ቅመም፤* ቍ 14፤ 5፥1:13፤ 6፥2፤ 8፥14 ይመ። ቅመም ከውጭ የሚመጣ የቅንጦት ሸቀጥ ነበር (1ነገ 10፥2:10:25፤ ሕዝ 27፥22 ይመ)። መልካም መዐዛ ይኖራቸው ዘንድ በተቀደሰው መቅቢያ ዘይት (ዘፀ 25፥6፤ 30፥23-25፤ 35፥8) እና በጣፋጭ ዕጣን ውስጥ ቅመም ይጨመር ነበር (ዘፀ 25፥6፤ 35፥8)፤ ሽቱም ውስጥ እየተቀላቀለ ያገለግል ነበር።

4፥11 *ከንፈሮችሽ የማር ወለላ ያንጠባጥባሉ፤* ሙሽራው ለሙሽራዪቱ ያለውን ጥልቅ ፍቅር እየገለጸላት ነው (ከምሳ 5፥3፤ 16፥24 ጋር ያነጻጽሩ)። በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ የነበሩ ሰዎች ጣፋጭነትን ፍቅር ከሚሰጠው ደስታ ጋር ያያይዙት ነበር። *ወተትና ማር፤* የተስፋዪቱን ምድር የሚያስታውስ አገላለጽ ሊሆን ይችላል (የዘፀ 3፥8 ማብ ይመ)። *ከአንደበትሽም፤* ኢዮ 20፥12፤ መዝ 10፥7 ይመ።

4፥12 *የአትክልት ቦታ፤* ስሜት የሚማርክ ቦታ ነው (ቍ 16፥5፥1፤ 6፥2 እንዲሁም የ1፥6 ማብ ይመ)። *የታጠረ... የተከበበ...የታተመም፤* የፍቅረኛዋን ድንግልና ወይም ራሷ ለይታ ለባሏ ብቻ የምትጠብቅ መሆንዋን የሚያመለክቱ ተለዋጭ ዘይቤዎች ሊሆኑ ይችላሉ። *ምንጭ ... ፏፏቴ፤* መንፈስን

[13]ተክልሽ ሮማን፣
ምርጥ ፍሬዎች፣
ሄናና ናርዶስ ያሉበት ነው።
[14]እንዲሁም ናርዶስና ቀጋ፣
ጠጅ ሣርና ቀረፋ፣
የተለያዩ የዕጣን ዛፎች፣
ከርቤና እሬት፣
ምርጥ ቅመሞች ሁሉ አሉበት።
[15]አንቺ[a] የአትክልት ቦታ ፏፏቴ፣
ከሊባኖስ የሚወርድ፣
የፈሳሽ ውሃ ጕድጓድ ነሽ።

**ሙሽራዪቱ**

[16]የሰሜን ነፋስ ሆይ፤ ንቃ፤
የደቡብም ነፋስ ሆይ፤ ና!
መዐዛው ያውድ ዘንድ፣
በአትክልት ቦታዬ ላይ ንፈስ፤
ውዴ ወደ አትክልት ቦታው ይግባ፤
ምርጥ ፍሬዎቹንም ይብላ።

**ሙሽራው**

**5** እኅቴ ሙሽራዬ፣ ወደ አትክልት ቦታዬ መጥቻለሁ፤
ከርቤዬን ከቅመሜ ጋር ሰብስቤአለሁ፤
የማር እንጀራዬን ከነወለላው በልቻለሁ፤
ወይኔንና ወተቴንም ጠጥቻለሁ።

**ባልንጀሮቹ**

ወዳጆች ሆይ፤ ብሉ፤ ጠጡ፤
እናንት ፍቅረኞች ሆይ፤ እስክትረኩ ጠጡ።

**ሙሽራዪቱ**

[2]እኔ ተኝቻለሁ፤ ልቤ ግን ነቅቶአል፤
ስሙ! ውዴ በር ያንኳኳል፤ እንዲህ ይላል፤
"እኅቴ ወዳጄ፣ ርግቤ፣
አንቺ እንከን የሌለብሽ፤ ክፈቺልኝ፤
ራሴ በጤዛ፣
ጠጕሬም በሌሊቱ ርጥበት ረስርሶአል።"
[3]ቀሚሴን አውልቄአለሁ፤
ታዲያ እንዴት እንደ ገና ልልበስ?
እግሬን ታጥቤአለሁ፤
እንዴት እንደ ገና ላቈሽሸው?
[4]ውዴ እጁን በበሩ ቀዳዳ አሾለከ፤
ልቤም ስለ እርሱ ይታወክ ጀመር።
[5]ለውዴ ልከፍትለት ተነሣሁ፤
በከርቤ ነጠብጣብ የራሱት እጆቼ፣
በከርቤም ፈሳሽ የተነከሩት ጣቶቼ፣
የመወርወሪያውን እጀታ ያዙ።
[6]ለውዴ ከፈትሁለት፤
ውዴ ግን አልነበረም፤ ሄዶአል፤
በመሄዱም ልቤ ደነገጠ፤[b]
ፈለግሁት፤ ነገር ግን አላገኘሁትም፤
ጠራሁት፤ ነገር ግን አልመለሰልኝም።
[7]የከተማዪቱም ጠባቂዎች
በከተማዪቱ ውስጥ ሲዘዋወሩ አገኙኝ፤
እነዚህ የቅጥሩ ጠባቂዎች፣
ደበደቡኝ፤ አቈሰሉኝ፤
ልብሴንም ገፈፉኝ።
[8]እናንት የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት ሆይ፤
አማጥናችኋለሁ፤
ውዴን ካገኛችሁት፣
ምን ትሉት መሰላችሁ?
በፍቅሩ መታመሜን ንገሩት።

**ባልንጀሮቹ**

[9]አንቺ ከሴቶች ሁሉ የተዋብሽ ሆይ፤
ውድሽ ከሌሎች እንዴት ቢበልጥ ነው?
እስከዚህ የምትማጠኚንስ፣
ውድሽ ከሌሎች እንዴት ቢበልጥ ነው?

**ሙሽራዪቱ**

[10]ውዴ ፍልቅልቅና ደመ ግቡ ነው፤

4፥13 ማሕ1፥14፤ 7፥12
4፥14 ዘፀ30፥23፤ ዘኍ24፥6፤ ማሕ1፥12፤3፥6
4፥15 ምሳ5፥18፤ ኢሳ27፥2፤58፥11፤ ኤር31፥12
4፥16 ቍ10:12፤ ማሕ2፥3፤7፥13
5፥1 ማሕ4፥8:11:12፤ኢሳ55፥1፤ ኢዩ3፥18
5፥2 ማሕ1፥15፤ 4፥7፤6፥9
5፥5 ቍ13
5፥6 ማሕ3፥1፤ 6፥1:2
5፥7 ማሕ3፥3
5፥8 ማሕ1፥14፤ 2፥5:7
5፥9 ማሕ1፥8
5፥10 መዝ45፥2

[a]15 ወይም እኔ ሙሽራዪቱ የተናገረችው
[b]6 ወይም በተናገረ ጊዜ ልቤ ወደ እርሱ ሄደ

ያድሳል፤ ደስታን ይሰጣል፤ ያዝናናልም። በምሳ 5፥15-20 ላይ እንደ ተጠቀሰው ምናልባት ሙሽራዪቱ በተቃራኒ ጾታነት ባላቸው ግንኙነት አጋር የሙሽራው በመሆኗ ሙሽራው ይህን ለመግለጽ የተጠቀመባቸው ተለዋጭ ዘይቤዎች ናቸው።

*4፥13-15፤* ቍ13-14 በቍ 12 ላይ ስለ ተጠቀሰው የአትክልት ቦታ፣ ቍ 15 ደግሞ በዚያው ክፍል ስለ ተጠቀሰው ፏፏቴ ያብራራሉ። በቍ 13-14 ላይ የተጠቀሱት ዛፎችና ቅመሞች በአብዛኛው ከውጭ የተገኙ ሲሆን፣ እነርሱም የሙሽራዪቱን ውበት ያመለክታሉ።

4፥13 *ተክልሽ፤* ወዳጁ ደስ የሚሰኝበትን የፍቅረኛዋን ሁኔታ ሁሉ ያሳያል። *ሄና፤* የ1፥14 ማብ ይመ። ናርዶስ፤ የ1፥12 ማብ ይመ።

4፥14 *ቀጋ፤* ሐምራዊ ወይም ነጭ አበባ የሚያወጣ ተክል ነው፤ አበባው በሚደርቅበት ጊዜ የወጥ ቅመም ሆኖ ያገለግል ነበር። *ጠጅ ሣር፤* በተቀደሰው መቅቢያ ዘይት (ዘፀ30፥23:25) እና በዕጣን ውስጥ (ኢሳ 43፥23-24) እየተጨመረ ሥራ ላይ የሚውል፣ መልካም መዐዛ ያለውና ከውጭ የሚመጣ (ኤር 6፥20 ይመ) ቅመም ነበር። *ቀረፋ፤* በተቀደሰ የመቅቢያ ዘይት ውስጥ ይጨመር ነበር (ዘፀ 30፥23:2)። *ከርቤ፤* የ1፥13 ማብ ይመ። *እሬት፤* ንጉሣውያን ቤተ ሰቦች የሚለብሷቸው የሰርግ ልብሶች ጥሩ ሽታ እንዲኖራቸውና ይጠቀሙበት ነበር (መዝ 45፥8)። ጋለሞቶችም መኝታቸው ጥሩ ሽታ እንዲኖረው በከርቤ፣ በእሬትና በቀረፋ ይጠቀሙ እንደ ነበር በምሳ7፥17 ላይ ተጠቅሶአል።

4፥15 *የፈሳሽ፤* በአንድ ቦታ ያልተከማቸ የምንጭ ውሃ ነው። *ከሊባኖስ የሚወርድ፤* በሊባኖስ ተራሮች ላይ ካለው የበረዶ ቍልል የሚወርድ ንጹሕ፣ ቀዝቃዛና ኵልል ብሎ የጠራ ውሃ ነው።

*4፥16፤* በፍቅር ደስ ይለን ዘንድ፣ የውበቴ መልካም ሽታ ውዴን ጠርቶ እንዲያመጣልኝ አየሩን ያውድ። *በአትክልት ቦታዬ፤* የእርሱ መሆኗንና ራሷን ለወዳጇ መስጠቷን የሚያመለክት ነው (6፥2 ይመ)።

5፥1 ሙሽራዪቱ ለሙሽራው እንደ አትክልት ቦታው የእርሱ ስለ ሆነች፣ በፍቅሯ እንደሚረካ ይናገራል። *እኅቴ፤* የ4፥9 ማብ ይመ። *ወዳጆች ሆይ ብሉ ...፤* የፍቅረኞቹ ባልንጀሮች ከፍቅር የመነጨ ደስታቸውን ይገልጻሉ።

*5፥2-8፤* 3፥1-5 እና የ3፥1 ማብ ይመ።

5፥2 *እኔ ተኝቻለሁ ... ነቅቶአል፤* ገና ልጅ የወለደች እናት የሕፃኗን አነስተኛ ድምፅ ለመስማት ጆሮዋን አንቅታ እንደምትተኛ ሁሉ፣ ፍቅር በእንቅልፍ ጊዜ እንኳ ሙሉ በሙሉ አያስተኛም።

*5፥3፤* የፍቅር ቋንቋ ሳይኖር በደመ ነፍስ የሚሰጥ ምላሽ ዐጕል መልጉምጉም ያስከትላል።

5፥5 *እጆቼ በከርቤም ፈሳሽ፤* ከከፍተኛ የፍቅር ስሜት የተነሣ፣ የሙሽራዪቱ እጆች ሽቱ በሽቱ ሆነዋል።

*5፥9፤* የሙሽራዪቱ ጓደኞች የጠየቁት ጥያቄ ሙሽሪት የወዳጇን ውበት እንድትገልጽ መንገድ ከፈተላት፤ ይህም የተጠቀሰው በዚህ ስፍራ ብቻ ነው።

5፥10 *ደመ ግቡ፤* 1ሳሙ 16፥12 ይመ።

ከዐሥር ሺሆችም የሚልቅ ነው።
[11]ራሱ የጠራ ወርቅ፣
ጠጕሩ ዞማ፣
እንደ ቍራም የጠቈረ ነው።
[12]ዐይኖቹ፣
በጅረት አጠገብ እንዳሉ ርግቦች፣
በወተት የታጠቡ፣
እንደ ዕንቍም ጕብ ጕብ ያሉ ናቸው።
[13]ጕንጮቹ የሽቱ መዐዛ የሚያመጡ፣
የቅመማ ቅመም መደቦችን ይመስላሉ፤
ከንፈሮቹም ከርቤ እንደሚያንጠባጥቡ፣
ውብ አበቦች ናቸው።
[14]ክንዶቹ በዕንቍ ፈርጥ ያጌጠ፣
የወርቅ ዘንግን ይመስላሉ፤
ሰውነቱም በሰንፔር ፈርጥ* ያጌጠ፣
አምሮ የተሠራ የዝሆን ጥርስን
ይመስላል።
[15]እግሮቹ በንጹሕ ወርቅ መቆሚያ ላይ
የተተከሉ፣
የዕብነ በረድ ምሰሶዎችን ይመስላሉ፤
መልኩ እንደ ሊባኖስ ነው፤
እንደ ዝግባ ዛፎቹም ምርጥ ነው።
[16]አፉ ራሱ ጣፋጭ ነው፤
ሁለንተናውም ያማረ ነው፤
እናንተ የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት ሆይ፤
ውዴ ይህ ነው፤ ባልንጀራዬም እርሱ
ነው።

## ባልንጀሮቿ

**6** አንቺ ከሴቶች ሁሉ የተዋብሽ ሆይ፤
ውድሽ ወዴት ሄደ?
አብረንሽም እንድንፈልገው፣
ውድሽ የሄደው በየት በኩል ነው?

## ሙሽራዪቱ

[2]ውዴ መንጋውን ለማሰማራት፣
ውብ አበቦችንም ለመሰብሰብ፣
የቅመማ ቅመም መደቦቹ ወዳሉበት፣
ወደ አትክልት ቦታው ወርዷል።
[3]እኔ የውዴ ነኝ፤ ውዴም የእኔ ነው፤
መንጋውንም በውብ አበቦች መካከል
ያሰማራል።

## ሙሽራው

[4]ውዴ ሆይ፤ አንቺ እንደ ቴርሳ የተዋብሽ፣
እንደ ኢየሩሳሌም ያማርሽ፣
ዐርማቸውን እንደ ያዙ ወታደሮችም
ግርማን የተጐናጸፍሽ ነሽ።
[5]አስጨንቀውኛልና፣
እባክሽ ዐይኖችሽን ከእኔ ላይ አንሺ፤
ጠጕርሽ ከገለዓድ ተራራ የሚወርድ፣
የፍየል መንጋ ይመስላል።
[6]ጥርሶችሽ
ከመታጠቢያ እንደ ወጡ የበግ መንጋ
ናቸው፤
ሁሉም መንታ መንታ የወለዱ፣
ከመካከላቸውም መካን የሌለባቸው
ናቸው።
[7]ከመሸፈኛሽ ውስጥ ያሉት ጕንጮችሽ፣
ለሁለት የተከፈለ ሮማን ይመስላሉ።
[8]ሥልሳ ንግሥቶች፣
ሰማንያ ቁባቶች፣
ቍጥራቸውም የበዛ ደናግል ሊኖሩ
ይችላሉ፤
[9]እንከን የሌለባት ርግቤ ግን ልዩ ናት፤
እርሷ ለወለደቻት የተመረጠች፤
ለእናቷም አንዲት ናት፤
ቈነጃጅት አይተው "የተባረክሽ ነሽ"

*14 ወይም ላፒስ ላዙሊ

5፥12 ዘፍ49፥12፤ ማሕ1፥15
5፥13 ቍ5፤ ማሕ1፥10፤2፥16፥2
5፥14 ኢዮ28፥6
5፥15 1ነገ4፥33፤ ማሕ7፥4
5፥16 ማሕ1፥5፤ 4፥3፤7፥9
6፥1 ማሕ1፥8፤5፥6
6፥2 ማሕ4፥12፤ 5፥6፡13
6፥3 ማሕ2፥16፤ 7፥10
6፥4 ዘኍ1፥52፤ ኢሱ12፥24፤1ነገ 15፥33፤መዝ48፥2፤ 50፥2
6፥5 ማሕ4፥1
6፥6 ማሕ4፥2
6፥7 ዘፍ24፥65፤ ማሕ4፥3
6፥8 ዘፍ22፥24፤ አስ2፥14፤መዝ45፥9
6፥9 ማሕ1፥15፤ 3፥4፤5፥2

5፥11 *የጠቈረ፤* የፍቅረኛዋም ጠጕሩ ጥቍር ነበረ (የ4፥1 ማብ ይመ)።

5፥12 *ርግቦች፤* የ1፥15 ማብ ይመ። *በጅረት አጠገብ፤* የሙሽራው ዐይኖች ብሩህ እንደ ሆኑ ያመለክታል። *በወተት የታጠቡ፤* የዐይኑን ነጭ ክፍል ይገልጻል።

5፥13 *ቅመም ... አበቦች፤* የሚቀጥሉት ተነጻጻሪና ተለዋጭ ዘይቤዎች በከፊል እንደሚያሳዩት፣ እነዚህ ተነጻጻሪ ዘይቤዎችም መልክን ሳይሆን፣ ስሜታዊ የሆኑ ነገሮችን ያነጻ ጽሩ ይሆናል። *አበቦች፤* የ2፥1 ማብ ይመ። *ከርቤ እንደሚያ ንጠባጥቡ፤* የፍቅር ስሜት በሙሽራው ከንፈር ተቀስቅሶአል።

5፥14 *የዕንቍ ፈርጥ፤* የሕዝ 1፥16 ማብ ይመ።

5፥15 *መልኩ እንደ ሊባኖስ፤* የተከበረና ግርማ ሞገስ ያለው መሆኑን ያመለክታል። *እንደ ዝግባ ዛፎችም ምርጥ ነው፤* የሊባኖስ ዝግባዎች በጥንት የመካከለኛው ምሥራቅ አገሮች ሁሉ የታወቁ ነበሩ፤ ከእነዚህም የሚገኘው ዕንጨት ቤተ መቅደሶችንና ቤተ መንግሥቶችን ለማስጌጥ ይጠቅም ነበር።

5፥16 *አፉ፤* የሙሽራውን አሳሳምና የፍቅር አነጋገሩን ያመለክታል። *የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፤*የ1፥5 ማብ ይመ።

*6፥1፤* በጓደኞች የቀረበው ጥያቄ ሙሽራዪቱ የወዳጇን ቍንጅና ከማገለጽ፣ በመካከላቸው ያለውን የፍቅር ግንኙነት በደ ስታ ወደ መቀበልና ይህም ግንኙነት ልዩ ግንኙነት እንዲሆን መሸጋገሪያ ፈጥሮአል።

6፥2 *ወደ አትክልት ቦታው፤* ፍቅረኛዋን ያመለክታል። *የቅመማ ቅመም መደቦቹ፤* ማራኪ የሆነውን ቍንጅናዋን ያመለ ክታል (ከ5፥13 ጋር ያነጻጽሩ)። *ለማሰማራት፤* ይህን የሚያደር ገው ራሱን ለማዝናናት ነው (የ2፥16 ማብ ይመ)። *አበቦችንም ለመሰብሰብ፤* የ2፥1 ማብ ይመ። ከፍቅረኛው ጋር ባለው የጠበቀ የፍቅር ግንኙነት የሚደሰት ወዳጅ፣ ሁከት በሌለበት ከፍተኛ የደ ስታ ስሜት ውስጥ ሆና ከአበባ ወደ አበባ እየሄደች ከምትበላው ሚዳቋ ጋር (የ2፥7፡9 ማብ ይመ) ተነጻጽሮአል።

6፥3 *እኔ ... የእኔ፤* የ2፥16 ማብ ይመ። አባባሉ ተገለ ባብጦ መነገሩን አስተውል፤ እዚህ ላይ ፍቅረኛዋ ለወዳጇ ራሷን መስጠቷ በአጽንዖት ተገልጾአል።

6፥4 *ቴርሳ፤* ማእከላዊ ቦታ ላይ የሚገኝ ጥንታዊ የከነዓን ከተማ ነው (ኢሱ12፥24 ይመ)። ቀዳማዊ ኢዮርብዓም (930-909 ቅ.ል.ክ) የሰሜኑ መንግሥት የመጀመሪያው መናገሻ ከተማ እንዲ ሆን መርጦት ነበር (1ነገ 14፥17፤ 1ነገ 15፥21፡16፥23-24 ይመ)። "ደስታ"፣"ውበት" የሚለው የስሙ ትርጒም ከተማው ውብ መሆኑን ይጠቁማል። ጸሓፊውም ይህን ቃል ከኢየሩሳሌም ጋር ጐን ለጐን ማስቀመጡም ለዚሁ ሳይሆን አይቀርም። በጥንት የመካከለኛ ምሥራቅ አገሮች ከተሞችን በሴት ፆታ መግለጽ (የ2ነገ 19፥21 ማብ ይመ) የተለመደ ስለ ነበር፣ የሙሽራዪቱን ውበት ከከተሞች ውበት ጋር ማነጻጸር እንግዳ ላይሆን ይችላል። *ግርማን የተጐናጸፍሽ፤* ቍ 10 ይመ። *ዐርማቸውን እንደ ያዙ ወታደ ሮችም፤* ሰንደቅ ዐላማ በመያዝ ተሰልፎ መሄድ የወታደርን ስሜት እንደሚያነሣሣ ሁሉ፣ የፍቅረኛዋም ውበት የወዳጇን ስሜት ያነሣሣል።

*6፥5-7፤* 4፥1-3እና ማብ ይመ።

6፥5 *አስጨንቀውኛልና ... ዐይኖችሽን፤* የሙሽራዪቱ ዐይኖች ሙሽራው የፍቅር ምርኮኛ እስኪሆን ድረስ ከፍተኛ የፍቅር ስሜት በውስጡ እንዳሳደሩበት ይገልጻል (4፥9 ይመ)።

*6፥8 ንግሥቶች... ቁባቶች ... ደናግል፤* በግዛቱ ውስጥ የሚገኙ መልከ መልካም ሴቶችን ወይም የሰሎሞን ቁባቶች የሚ ያመለክት ይሆናል።

6፥9 *አንዲት ናት፤* አንድ ብቻ መሆን ለማሳየት ሳይሆን፣ በተለየ ሁኔታ መወደዷን ለማመልከት ነው (ከዘፍ 22፥2፤ ከመሳ 11፥34፤ ከምሳ 4፥3 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቈነጃጅት ...*

አሏት፤
ንግሥቶችና ቁባቶችም አመሰገኗት።

**ባልንጀሮቿ**

[10]እንደ ንጋት ብርሃን ብቅ የምትል፣
እንደ ጨረቃ የደመቀች፣ እንደ ፀሓይ
ያበራች፣
ዐርማ ይዞ በሰልፍ እንደ ወጣ ሰራዊት
ግርማዋ የሚያስፈራ ይህች ማን ናት?

**ሙሽራው**

[11]በሸለቆው ውስጥ አዲስ የበቀሉትን
አትክልቶች ለማየት፣
ወይኑ ማቈጥቈጡን፣
ሮማኑ ማበቡን ለመመልከት፣
ወደ ለውዙ ተክል ቦታ ወረድሁ።
[12]ይህን ከማወቄ በፊት፣
ምኞቴ በሕዝቤ ንጉሣዊ ሠረገሎች
መካከል[a] አስቀመጠኝ።

**ባልንጀሮቿ**

[13]አንቺ ሱላማጢስ ሆይ፤ ተመለሺ፤
ኧረ ተመለሺ፤
እንድናይሽ ተመለሺ፤ እባክሽ ተመለሺ።

**ሙሽራው**

የመሃናይምን ዘፈን እንደሚመለከት
ሰው፣
ሱላማጢስን የምትመለከቷት ለምንድን
ነው?

**7** አንቺ የልዑል ልጅ ሆይ፤
ነጠላ ጫማ የተጫሙ እግሮችሽ
እንዴት ያምራሉ!
ሞገስን የተጐናጸፉ ዳሌዎችሽ፣
ብልኀ አንጥረኛ የተጠበባቸውን
የዕንቍ ሐብል ይመስላሉ።
[2]ዕንብርትሽ ጥሩ የወይን ጠጅ እንደ
ማይጐድልበት፣
እንደ ክብ ጽዋ ነው፤
ወገብሽ ዙሪያውን በውብ አበባ የታሰረ
የስንዴ ክምር ይመስላል።
[3]ሁለቱ ጡቶችሽ፣
መንታ የዋልያ ግልገሎችን ይመስላሉ።
[4]ዐንገትሽ በዝሆን ጥርስ እንዳጌጠ
መጠበቂያ ማማ ነው፤
ዐይኖችሽ በባትረቢ በር አጠገብ
እንዳሉት፣
እንደ ሐሴቦን ኵሬዎች ናቸው፤
አፍንጫሽ ወደ ደማስቆ አቅጣጫ
እንደሚመለከት፣
እንደ ሊባኖስ መጠበቂያ ማማ ነው።
[5]የራስሽ ቅርጽ እንደ ቀርሜሎስ ተራራ
አክሊል ሆኖልሻል፤
ጠጕርሽ የሐር ጕንጕን የመሰለ ነው፤
ንጉሡም በሹሩባሽ ታስሮ ተይዞአል።
[6]እንዴት ውብ ነሽ! እንዴትስ ደስ የምትይ
ነሽ!
ፍቅሬ ሆይ፤ የምታስደስቺ ነሽ።
[7]ቁመናሽ እንደ ዘንባባ ዛፍ መለል ያለ
ነው፤
ጡቶችሽም የፍሬውን ዘለላ ይመስላሉ።
[8]እኔም፣ "የዘንባባውን ዛፍ እወጣለሁ፤
ዘለላዎቹንም እይዛለሁ" አልሁ።
ጡቶችሽ የወይን ዘለላ፣
የእስትንፋስሽም መዐዛ እንደ እንኰይ
ፍሬ ይሁኑ፤
[9]ከናፍሮችሽም እንደ ማለፊያ የወይን ጠጅ
ይጣፍጡ።

**ሙሽራዪቱ**

የወይን ጠጁ በቀስታ እየተንቈረቈረ፣
ወደ ውዴ ከንፈሮችና ጥርሶች
ይውረድ።[†]

6፥11 ማሕ7፥12
6፥13 ዘፀ15፥20
7፥1 መዝ45፥13
7፥3 ማሕ4፥5
7፥4 ዘኍ21፥26፤ መዝ144፥12፤ ማሕ5፥15
7፥5 ኢሳ35፥2
7፥6 ማሕ 4፥10
7፥7 ማሕ4፥5
7፥8 ማሕ2፥5
7፥9 ማሕ5፥16

[a]12 ወይም ከአሚናዳብ ሠረገሎች መካከል፡ወይም ከልዑል ሕዝቦች ሠረገሎች መካከል
[†]9 ሰብዓ ሊቃናት፣አቍሚላ፣ሽልጌትና ሱርስት እንዲሁ ሲሆኑ ዕብራይስጡ ግን ወደ ተኙ ሰዎች ከንፈሮች ይላል

*እመሰገኗት፤* ሌሎች ሴቶች ሁሉ ውበቷን አደነቁ (1፥8፤5፥9፤ 6፥1 ይመ)።

*6፥10፤* 5፥9፤6፥1 ይመ።

6፥11 *በሸለቆው ውስጥ ... ለማየት፤* ጊዜው ጸደይ መሆኑን ያመለክታል (የ2፥11-13ማብ ይመ)።

6፥12 በዚህ መጽሐፉ ካሉት ጥቅሶች ይህ ጥቅስ ለመረዳት እጅግ አስቸጋሪ ነው። *ሠረገሎች፤* ሰሎሞን በሠረገሎች በጣም የታወቀ ነበር (1ነገ 10፥26)።

6፥13 *ሱላማጢስ፤* ሙሽራዪቱ ሱነማዪት ወይም "የሰሎሞን" መሆኗን ያመለክታል።

*7፥1-7፤* እዚህ ላይ ገለጻው ከራስ ጀምሮ ወደ እግር የሚወርድ ሳይሆን፣ ከእግር ወደ ራስ የሚወጣ ነው (ከ5፥11-15 ጋር ያነጻጽሩ)።

7፥1፤ ከቍ6 ጋር ያነጻጽሩ። *የልዑል ልጅ፤* የውበቷን ማራኪነት ይገልጻል (መዝ 45፥13 ይመ)።

7፥2 *ጽዋ፤* ሁለት እጀታ ያለው መቀመጫው ክብ የሆነ ትልቅ ዋንጫ መሳይ ዕቃ ነው (ዘፀ 24፥6፤ ኢሳ22፥24፤ አሞ 6፥6 ይመ)። *አበባ የታሰረ፤* ሙሽራዪቱ በወገቧ ዙሪያ የአበባ ጌጥ ማድረጓን ሊያመለክት ይችላል።

*7፥3፤* የ4፥5 ማብ ይመ።

7፥4 *በዝሆን ጥርስ እንዳጌጠ መጠበቂያ ማማ፤* የአንድን ነገር ቅርጽ፣ ቀለምና አሠራር የሚያመለክት ሥዕላዊ አገላለጽ ነው። *ባትረቢ፤* ትርጕም "የብዙዎች ሴቶች ልጅ" ማለት ነው። በሐሴቦን የታወቀ ስም ሳይሆን አይቀርም። እንደ *ሊባኖስ መጠበቂያ ማማ፤* በሰሎሞን ግዛት ሰሜናዊ ድንበር ላይ የሚገኝ፣ ለወታደራዊ አገልግሎት የተሠራ ቅጥር ሊሆን ይችላል፤ ነገር ግን እጅግ የሚያምረውንና ከፍተኛ የሆነውን የሊባኖስን የተራራ ሰንሰለት የበለጠ የሚያመለክት ይመስላል። *ሐሴቦን፤* ቀደም ሲል የንጉሥ ሲዖን መናገሻ ከተማ ነበረች (ዘኍ 21፥26)፤ በጸደይ ወራት ከፍተኛ የውሃ መጠን ታገኝ ነበር። *ኵሬዎች፤* የሙሽራይቱ ዐይኖች እንደ ኵሬ ውሃ ያንጸባርቃሉ፤ ይህ ሥዕላዊ አገላለጽ ጨዋነትንና ሰላማዊነትን የሚያሳይ ሊሆን ይችላል።

7፥5 *ቀርሜሎስ ተራራ፤* በግዛቱ ምዕራባዊ ዳርቻ መካከለኛ ቦታ ላይ የሚገኝ ከፍተኛ ቦታ ሲሆን፣ ጫፉም ላይ ዛፎች ያሉበት እጅግ የሚያምር ስፍራ ነው። *የሐር ጕንጕን፤* በ3፥10 ላይ እንደ ተጠቀሰው፣ ቀለሙ ሐምራዊ የሆነ የንጉሥ ቤተ ሰብ ልብስ ነው (የዘፀ 25፥4 ማብ ይመ)። *በሹሩባ፤* የዕብራይስጡ ቃል ከሚፈስ ውሃ ጋር እንደሚመሳሰል ይጠቍማል (ከ4፥1፤ 6፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

7፥7 *የዘንባባ፤* የተምር ዛፍ ነው።

7፥8 *እኔም ... አልሁ፤* ለራሱ መናገሩን ያመለክታል። *እወጣለሁ፤* ሊቈጣጠረው በማይችለው ሁኔታ በፍቅረኛው ውበት መማረኩን ያሳያል። *እንኰይ፤* ከአበባዎቹ የሚወጣውን መልካም መዐዛ ሊያመለክት ይችላል (ነገር ግን የ2፥3 ማብ ይመ)።

7፥9 *የወይን ጠጅ ... ውዴ፤* ሙሽራዪቱ እንደ ወይን ጠጅ የሚጣፍጠውን (5፥1) ፍቅሯን ለሙሽራው ትሰጣለች።

[10]እኔ የውዴ ነኝ፤
 የእርሱም ምኞት እኔው ነኝ::
[11]ውዴ ሆይ፤ ና ወደ ገጠር እንሂድ፤
 ወደ መንደርም[*] ገብተን እንደር፤
[12]ማልደን ወደ ወይኑ ተክል ቦታ እንሂድ፣
 ወይኑ እንቡጥ አውጥቶ፣
አበባው ፈክቶ፣
 ሮማኑ አፍርቶ እንደ ሆነ እንይ፤
 በዚያም ራሴን በፍቅር እሰጥሃለሁ::
[13]ትርንጉዎች መዐዛቸውን ሰጡ፤
 አዲስ የተቀጠፈውም ሆነ የበሰለው፣
ጣፋጩ ፍሬ ሁሉ በደጃፋችን አለ፤
 ውዴ ሆይ፤ ለአንተ አስቀምጬልሃለሁ::

# 8

ምነው አንተ የእናቴን ጡት እንደ ጠባ፣
እንደ ወንድሜ በሆንህ!
 ከዚያም ውጭ ባገኝህ፣
እስምህ ነበር፤
 ታዲያ ማንም ባልናቀኝ!
[2]እኔም ወደ አስተማረችኝ፣
 ወደ እናቴም ቤት፣
እጅህን ይዤ በወሰድሁህ ነበር፤
 የምትጠጣውን ጣፋጭ የወይን ጠጅ፣
 የሮማኔን ጭማቂም በሰጠሁህ::
[3]ግራ እጁን ተንተርሻለሁ፤
 ቀኝ እጁም ዐቅፎኛል::
[4]እናንት የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት፤
 ራሱ እስኪፈልግ ድረስ፣
ፍቅርን እንዳታስነሡት ወይም
 እንዳትቀሰቅሱት አማጥናችኋለሁ::

## ባልንጀሮቿ

[5]ውዷን ተደግፋ፣
 ከምድረ በዳ የምትወጣ ይህች ማን ናት?

## ሙሽራዪቱ

 ከእንኰይ ዛፍ ሥር አስነሣሁህ፤
በዚያ እናትህ ፀነሰችህ፤
 በዚያም ታምጥ የነበረችው አንተን ወለደችህ::
[6]በልብህ እንዳለ፣
 በክንድህም እንደምትይዘው ማኅተም አስቀምጠኝ፤
ፍቅር እንደ ሞት የበረታች፣
 ቅናቷም[1] እንደ መቃብር[2] ጨካኝ ናትና፤
እንደሚንበገበግ እሳት፣
 እንደ ኀይለኛም ነበልባል ትነዳለች::[3]
[7]የውሃ ብዛት ፍቅርን ሊያጠፋ አይችልም፣
 ፈሳሾችም አያስጥሟትም፤
ሰው የቤቱን ሀብት ሁሉ
 ስለ ፍቅር ቢሰጥ
 ፈጽሞ ይናቃል::

## ባልንጀሮቿ

[8]ትንሽ እኅት አለችን፤
 ጡትም ገና አላወጣችም፤
ስለ እርሷ በምንጠየቅበት ቀን
 ምን ማድረግ እንችል ይሆን?
[9]እርሷ ቅጥር ብትሆን፣
 በላይዋ የብር መጠበቂያ ማማ
 እንሠራባታለን፤
በር ብትሆን፣
 በዝግባ ዕንጨት እንከልላታለን::

7፥10 መዝ45፥11፤ ማሕ2፥16፤6፥3
7፥12 ማሕ1፥6፤ 2፥13፡15፤ 4፥13፤6፥11
7፥13 ዘፍ30፥14፤ ማሕ4፥16
8፥2 ማሕ3፥4
8፥3 ማሕ2፥6
8፥4 ማሕ2፥7፤3፥5
8፥5 ማሕ3፥4፡6
8፥6 ዘኍ5፥14፤ ማሕ1፥ 2
8፥7 ምሳ6፥35

[*]11 ወይም *ወደ ሄና ቍጥቋጦች*
[1]6 ወይም *ኀይለኛ ስሜት*
[2]6 ዕብራይስጡ *ሲኦል ይለዋል*
[3]6 ወይም *እንደ እግዚአብሔር ነበልባል*

7፥12 *ራሴን በፍቅር እሰጥሃለሁ፤* ራሷን ሙሉ በሙሉ ለወዳጇ ትሰጣለች::

7፥13 *ትርንጉዎች፤* አጭር ግንድ ያለውና ብዙ ፍሬ የሚያፈራ ተክል ነው (የዘፍ 30፥14 ማብ ይመ)፤ የአበባውም ሽታ ኀይለኛ ነው:: *በደጃፋችን፤* ፍቅረኞቹ የሚገናኙበት ስፍራ ነው:: *ጣፋጩ ፍሬ ሁሉ፤* ሙሽራዪቱ ከአትክልት ስፍራዋ ለሙሽራው የምትሰጠውን ደስ የሚያሰኝ ፍሬ የሚያሳይ ተለዋጭ ዘይቤ ነው (ከ4፥13-14 ጋር ያነጻጽሩ):: *አዲስ... የበሰለው፤* አስቀድሞ የተሰጠውንና ገናም ሊሰጥ ያለውን አስደሳች ነገር ያመለክታል::

8፥1 *ማንም ባልናቀኝ!፤* ሙሽራዪቱ ማንንም ሳታፍር ለሙሽራው ፍቅሯን በአደባባይ ትገልጻለች::

8፥2 *በሰጠሁህ፤* ሙሽራዪቱ ደስ የሚያሰኘውን ፍቅሯን ለወዳጇ ታቀርባለች:: *ጭማቂ፤* የዕብራይስጡ ቃል የሚያሰክር መጠጥ ያመለክታል::

*8፥4፤* 2፥7እና ማብ ይመ::

8፥5 *ከምድረ በዳ ... ማን ናት፤* 3፥6 ይመ:: *ከእንኰይ ዛፍ ሥር፤* በጥንት ዘመን የግብረ ሥጋ ግንኙነት ማድረግና ልጅ መውለድ ፍሬ ከሚሰጡ ዛፎች ጋር ተያይዞ ይነገር ነበር::

8፥6-7 *ፍቅር ... መቃብር፣ ነበልባል ትነዳለች:: የውሃ ብዛት ... ሊያጠፋ፤* እነዚህ ሦስት ጥበብ አዘል አነጋገሮች (ከመጽሐፈ ምሳሌ መግቢያ "የጥበብ መጻሕፍት" የሚለውን ይመ)፣ የጋብቻ ፍቅር በሰው ሕይወት ውስጥ ጠንካራና ጽኑ ኀይል እንዳለው ያመለክታሉ:: በእነዚህም የጥበብ አባባሎች ማሕልዩ መድፊያው ላይ ይደርሳል፤ ዐላማውንም ይፋ ያደርጋል::

8፥6 *ማኅተም፤* የተጻውአ ስም አንድን ሰው በግል እንደሚያመለክትና የከበረ እንደ ሆነ ሁሉ፣ ማኅተምም ለባለቤቱ እንደዚሁ የከበረ ዕቃ ነው (የዘፍ38፥18 ማብ ይመ):: *በክንድህም፤* በቅኔያዊ አነጋገር ከ"እጅ" ጋር ተመሳሳይ ነው:: *እንደ መቃብር ጨካኝ፤* መቃብር ሙታንን እንደማይለቅ ሁሉ፣ ፍቅርም የወደደውን ሰው አይለቅም:: ኀይለኛም ነበልባል፤ የዕብራይስጡ አገላለጽ በእግዚአብሔር የተቀጣጠለ ኀይለኛ የእሳት ነበልባልን ያሳያል::

8፥7 *የውሃ ብዛት፤* ይህ ሐረግ የውቅያኖስ ውሃ ብቻ ሳይሆን (መዝ 107፥23 ይመ)፤ በዓለም ሁሉ ጥፋት ያመጣሉ በማለት ጥንታዊ የመካከለኛ ምሥራቅ ሰዎች የፈሯቸውን ውሆች ጭምር ነው (መዝ32፥6 ይመ)፤ እነዚህ ውሆች ከሙታን ዓለም ጋር ተያይዘው ተጠቅሰዋል (የመዝ 30፥1 ማብ ይመ):: *ሰው ... ይናቃል፤* ፍቅር ዋጋ ሊተመንለት የማይቻል፣ ውድ ነገር እንደ ሆነ የሚገልጽ፣ አራተኛው የጥበብ አነጋገር ነው (የቍ6-7 ማብ ይመ)::

*8፥8-14፤* በማሕልዩ ማጠቃለያ ላይ የጓደኞቿ ቃል (ቍ 8-9)፣ ሙሽራዪቱ ስለ ወይን ቦታዋ የምትናገረው (ቍ 12) እና በመጨረሻም ስለ ወዳጇ የምትናገረው ቃል (ቍ11-12) ወደ መዝሙሩ የመጀመሪያ ሐሳብ መመለስን ያሳያል (1፥2-7 ይመ):: ይህ ክፍል ሙሽራዪቱ ለፍቅርና ለጋብቻ እንዲሁም ከወዳጇ ጋር ባላት የፍቅር ግንኙነት ፍሬ ለማፍራት መድረሷን የሚያመለክት ነው::

*8፥8፤* በጥንት የቅርብ ምሥራቅ አገሮች በተለይ የጋብቻን ጒዳይ በመከታተል ረገድ ወንድሞች ለእኅቶቻቸው ኀላፊ ይሆኑ ነበር (ዘፍ 24፥50-60፤ 34፥13-27 ይመ):: *ስለ እርሷም ... በምንጠየቅበት ቀን፤* ብዙውን ጊዜ የጋብቻ ስምምነት ለአካለ መጠን ከመድረስ በፊት ይደረግ እንደ ነበር ያመለክታል::

*8፥9፤* ይህ ጥቅስ ምናልባት ለፍቅርና ለጋብቻ ትክክለኛ ዕድሜ ላይ እስክትደርስ ድረስ፣ ለታናሽ እኅታቸው ጥንቃቄ ለማድረግ ወንድሞቿ ያላቸውን ቍርጥ ውሳኔ ሊያሳይ ይችላል:: ወይም ለጋብቻ ከመጠየቋ በፊት በሚገባ ያጌጠችና የተዘጋጀች ስለ መሆኗ ወንድሞቿ መከታተላቸውን የሚያመለክት ሊሆንም ይችላል::

**ሙሽራዪቱ**

[10]እነሆ፤ እኔ ቅጥር ነኝ፤
ጡቶቼም እንደ ማማ ግንቦች ናቸው፤
እኔም በዐይኖቹ ፊት፣
ሰላምን እንደሚያመጣ ሰው ሆንሁ።
[11]ሰሎሞን በብኤላሞን የወይን ተክል ቦታ ነበረው፤
የወይኑን ተክል ቦታም ለአትክልተኞች አከራየው፤
እያንዳንዳቸውም የፍሬውን ዋጋ፣
አንድ አንድ ሺህ ሰቅል ብር ያመጡለት ነበር።
[12]የወይኔ ተክል ቦታ የራሴ፣ የግሌ ነው፤
ሰሎሞን ሆይ፤ አንድ ሺሁ ሰቅል ለአንተ፤
ፍሬውን ለሚጠብቁ ደግሞ ሁለት መቶ ይሁን።

**ሙሽራው**

[13]አንቺ በአትክልቱ ቦታ የምትኖሪ ሆይ፤
ባልንጀሮቼ ድምፅሽን ይሰማሉ፤
እስቲ እኔም ልስማው።

**ሙሽራዪቱ**

[14]ውዴ ሆይ፤ ቶሎ ናልኝ፤
ሚዳቋን፣
ወይም በቅመም ተራራ ላይ የሚዘል፣
የዋልያን ግልገል ምሰል።

8፥11 መክ2፥4፤ ኢሳ7፥23
8፥12 ማሕ1፥6
8፥14 ምሳ5፥19፤ ማሕ2፥8፡9

8፥10 *እኔ ... እንደ መጠበቂያ ማማዎች፤* በወንድሞቿ ከምትጠበቅበት ጊዜ ይልቅ፣ አሁን ባደገች ጊዜ የበለጠ ደስ ይላታል (ሕዝ 16፥7-8ይመ)።

8፥11-12 *አንድ ሺህ ... ሁለት መቶ፤* እነዚህ ቍጥሮች ቃል በቃል (ኢሳ 7፥23 ይመ) የሚተረጐሙ ይሁኑ ወይም አይሁኑ የሚታወቅ ነገር የለም።

8፥11 *ኤላሞን፤* የት እንደሚገኝ አይታወቅም። አንዳንድ ትርጕሞች ይህንኑ ቃል፣ "ብአልሃሞን" ይሉታል፤ ሃሞን በዕብራይስጡ "ሀብት"ወይም "የተትረፈረፈ ብልጽግና" ማለት ሲሆን፣ በኣል ማለት ደግሞ ጌታ ማለት ነው፤ ስለዚህ "በኣል ሃሞን" ማለት፣ "የብልጽግና ጌታ" ማለት ሊሆን ይችላል፤ ይኸውም የሰሎሞንን የተትረፈረፈ ብልጽግና የሚያመለክት ነው።

8፥12 *የወይኔ ተክል ቦታ የራሴ የግሌ ነው፤* ሰውነቷን ያመለክታል (የ1፥6 ማብ ይመ)። *የራሴ፤* ሰሎሞን የራሱ የወይን ቦታ ባለቤት እንደ ሆነ ሁሉ፣ ሙሽራዪቱም እንደ ፈቀደች ልትሰጥ የውበቷ ባለቤት ናት።

8፥13 *በአትክልቱ ቦታ፤* በ7፥11-12 ላይ ሙሽራዪቱ ወዳጇን ወደ ገጠርና ወደ ወይኑ ቦታ አብሮአት እንዲሄድ ትጋብዘዋለች። ይህ ምሳሌያዊ አነጋገር ሙሽራዪቱ በአትክልቱ ውስጥ በተገቢው ቦታ መሆኗን ያሳያል። *ባልንጀሮቼ፤* የወዳጇ ጓደኞች ሊሆኑ ይችላሉ (1፥7 ይመ)። *እስቲ እኔም ልስማው፤* 2፥14 ይመ።

8፥14 *ሚዳቋን ወይም ... የዋልያን ግልገል ምሰል፤* ሙሽራዪቱ ደስ ይላት ዘንድ የወንድነት ጥንካሬንና ፍጥነትን አሳይ ማለት ነው (የ2፥9 ማብ ይመ)። *በቅመም ተራራ ላይ፤* ከ2፥17 ጋር ያነጻጽሩ።

# ትንቢተ ኢሳይያስ

## መግቢያ

### ጸሐፊው፤

የአሞጽ ልጅ ኢሳይያስ፣ ትንቢት ከጻፉ ታላላቅ ነቢያት መካከል እንደ ዋነኛ ይቈጠራል። የስሙ ትርጉም፣ "እግዚአብሔር ያድናል" ማለት ነው። ነቢዩ ኢሳይያስ የኖረው አሞጽ፣ ሆሴዕና ሚክያስ በነበሩበት ዘመን ነው፣ አገልግሎቱንም የጀመረው ንጉሥ ዖዝያን በሞተበት ዓመት በ740 ዓ.ቅ.ክ ነው። አንድ ተአማኒነቱ ያልተረጋገጠ፣ 'የኢሳይያስ ዕርገት' የተባለ የአይሁድ ትውፊት፣ ኢሳይያስ በንጉሥ ምናሴ ዘመን በመጋዝ ተሰንጥቆ እንደ ተገደለ ያመለክታል (ከዕብ11፥37 ጋር ያነጻጽሩ)። በትንቢት መጽሐፉ የነቢዩ ሚስት መፀነስ እንዲሁም ቢያንስ ቢያንስ ያሱብ (7፥3) እና ማኸር- ሻላል- ሐሽ- ባዝ (8፥3) የተባሉት ሁለቱ ልጆቹ መጠቀሳቸው ኢሳይያስ ባለ ትዳር እንደ ነበረ ያመለክታል። ነቢዩ ኢሳይያስ አብዛኛውን ዘመኑን በኢየሩሳሌም በተለይም ንጉሥ ሕዝቅያስን በመምከር እንዳሳለፈ ይገመታል (37፥1-2 ይመ)። በተጨማሪም የንጉሥ ዖዝያንን ዘመነ መንግሥት ታሪክ የጻፈው እርሱ ነው ተብሎ ይታመናል (2ዜና26፥22)።

ዛሬ ብዙ ምሁራን በኢሳይያስ ስም የሚታወቀውን የትንቢት መጽሐፍ ሙሉ በሙሉ ራሱ መጻፉን ይጠራጠራሉ፤ ይሁን እንጂ በተለያዩ የመጽሐፉ ክፍሎች (1፥1፤ 2፥1፤ 13፥1 ይመ) የነቢዩ ስም ብቻ በተደጋጋሚ መጠቀሱ ጸሐፊው ራሱ ለመሆኑ በቂ ማስረጃ ሊሆን ይችላል። ለመጽሐፉ የሐሳብ ወጥነት እንደ ዋና ማረጋገጫ ሆኖ የሚቀርበው ከምዕራፍ1-39 ዐሥራ ሁለት ጊዜ፣ ከምዕራፍ 40-66 ዐሥራ አራት ጊዜ የተጠቀሰው ለእግዚአብሔር የተሰጠው፣ "የእስራኤል ቅዱስ" የሚለው ስም ነው። ይህ መጠሪያ ከኢሳይያስ መጽሐፍ ውጪ፣ በሌሎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ ተጠቅሶ የሚገኘው ስድስት ጊዜ ብቻ ነው። ከዚህም በላይ በምዕራፍ1-39 እና በምዕራፍ 40-66 ላይ ባሉት ሁለት ክፍሎች እጅግ ተመሳሳይ የሆኑ ቃሎችና ሐረጎች ተደጋግመው ተጠቅሰዋል። የሚከተሉትን ክፍሎች ያነጻጽሩ፦

| | |
|---|---|
| 1፥2 | 66፥24 |
| 1፥5-6 | 53፥4-5 |
| 5፥27 | 40፥30 |
| 6፥1 | 52፥13፤ 57፥15 |
| 6፥11-12 | 62፥4 |
| 11፥1 | 53፥2 |
| 11፥6-9 | 65፥25 |
| 11፥12 | 49፥22 |
| 35፥10 | 51፥11 |

መጽሐፉን የተለያዩ ጸሐፊዎች ቢጽፉት ኖሮ በመጽሐፉ ውስጥ ባሉት ምዕራፎች ውስጥ የሚገኘውን ይህን የእግዚአብሔር ስም እንዲሁም ተመሳሳይ ቃሎችንና ሐረጎችን በመደጋገም ሊጠቅሱ አይችሉም ነበር።

ኢሳይያስ እሳትን የቅጣት ምሳሌ አድርጎ ማቅረቡ (1፥31፤ 10፥17፤ 26፥11፤ 33፥11-14፤ 34፥9-10፤ 66፥24)፣ በኢየሩሳሌም ያለውን "ቅዱስ ተራራ" ማመልከቱና (የ2፥2-4 ማብ ይመ) ወደ ኢየሩሳሌም የሚወስደውን አውራ መንገድ (የ11፥16 ማብ ይመ) መጥቀሱ፣ እነዚህ በመጽሐፉ ውስጥ ተደጋግመው የሚገኙ መሪ ሐሳቦች እንደ ሆኑ ያስገነዝባል።

በሌላ በኩል ደግሞ የመጽሐፉ አወቃቀር ራሱ ወጥነቱን ያመለክታል፤ ጸሐፊውም አንድ ሰው እንደ ሆነ የሚያሳይ ነው። በሌላ በኩል በም 36-39 ላይ ያለው ክፍል በም 1-35 ላለው ክፍል መዝጊያ ሲሆን፣ በም 40-66 ላለው ክፍል ደግሞ መግቢያ ሆኖ ይገኛል (የቍ 36፥1 ማብ ይመ)። በዚህም የመጽሐፉ ትረካ የተያያዘ እንጂ ወጥነት የጐደለው እንዳልሆነ እንመለከታለን።

አያሌ የአዲስ ኪዳን ጥቅሶች ከተለያዩ የመጽሐፉ ምዕራፎች ጋር በማገናኘት ነቢዩ ኢሳይያስን ይጠቅሳሉ፤ ለምሳሌ ማቴ 12፥17-21 (ከኢሳ42፥1-4)፤ ማቴ3፥3 እና ሉቃ3፥4 (ከኢሳ40፥3)፤ ሮሜ 10፥16፡20 (ከኢሳ53፥1፤ 65፥1)በተለይ፤ ዮሐ12፥38-41 (ከኢሳ53፥1፤ 6፥10)ጋር እንዴት እንደ ተጣቀሰ ማየት ይቻላል።

### የተጻፈበት ጊዜ

በም 1-39 ባለው ክፍል ከተፈጸሙት ድርጊቶች አብዛኛው በኢሳይያስ የአገልግሎት ዘመን የተከናወነ ነው (6፥1፤ 14፥28፤ 36፥1 ይመ)፤ ስለዚህ እነዚህ ምዕራፎች ተጽፈው የተጠናቀቁት ከ701 ዓ.ቅ.ክ በኋላ ብዙ ሳይቈይ እንደ ሆነ መገመት ይቻላል። የአሦር ሰራዊትም ሙሉ በሙሉ የተደመሰሰው በዚሁ ዘመን ነበር (የ10፥16 ማብ ይመ)። ነቢዩ ኢሳይያስ እስከ 681 ዓ.ቅ.ክ ድረስ ሳይኖር አይቀርም (የ37፥38 ማብ ይመ)፤ ይህ ከሆነም ነቢዩ በኋለኛው የዕድሜ ዘመኑ በም 40-66 ያለውን ክፍል ጽፎ ሊሆን ይችላል። ሐዋርያው ዮሐንስ በራእ 4-22 ላይ ወደ ፊት ስለሚሆነው ነገር እንደ ጻፈ ሁሉ ነቢዩ ኢሳይያስም በስድስተኛው ምዕተ ዓመት (ዓ.ቅ.ክ) ተማርከው ስለሚወሰዱትና ወደ ፊት ስለሚሆነው ነገር በማመልከት ጽፎአል።

### የመጽሐፉ ታሪካዊ ዳራ

ኢሳይያስ ትንቢቱን የጻፈው የአሦር መንግሥት ግዛቱን በከፍተኛ ደረጃ እያስፋፋ ባለበት ዘመንና የእስራኤል መንግሥት እየተዳከመ በሄደበት ዘመን ነበር:: አሦራውያን በንጉሥ ቴልጌልጌልፌልሶር ሣልሳዊ ዘመን (745-727 ዓ.ቅ.ክ) ወደ ምዕራብ አቅጣጫ ወደ ሶርያና ወደ ከነዓን በኀይል ተንቀሳቀሱ:: ይህን የአሦር ጦር እንቅስቃሴ ለመግታት በ733 ዓ.ቅ.ክ የሶርያና የእስራኤል ነገሥታት የይሁዳ ንጉሥ አካዝ እንዲተባበራቸው ሊያስገድዱት ሞከሩ:: ነገር ግን ውሳኔውን ነቢዩ ኢሳይያስ በጥብቅ ቢቃወመውም (የ7፥1 ማብ ይመ)፣ አካዝ የአሦር ንጉሥ ቴልጌልቴልፌልሶር እንዲረዳው ለመነ:: ስለዚህ አሦር ይሁዳን በመርዳት የሰሜኑን የእስራኤል መንግሥት በ722-721 ዓ.ቅ.ክ. ወርራ ያዘች:: ይህ ደግሞ ይሁዳን የበለጠ ለጥቃት አጋልጦአት በ701 ዓ.ቅ.ክ የአሦር ንጉሥ ሰናክሬም ራሷን ኢየሩሳሌምን ለመውጋት ወጣ (36፥1 እና ማብ ይመ):: እግዚአብሔርን ይፈራ የነበረው ንጉሥ ሕዝቅያስም አጥብቆ በጸለየ ጊዜ፣ ነቢዩ ኢሳይያስ አሦራውያን ከተማዪቱን ለቀው ይሄዱ ዘንድ እግዚአብሔር እንደሚያስገድዳቸው ትንቢት ተናገረ (37፥6-7)::

ነገር ግን ይሁዳ በኀጢአቷ ምክንያት በባቢሎናውያን እጅ እንደምትማረክ በማሳሰብ አስጠንቅቃት፤ የባቢሎን ንጉሥ መልእክተኞች ሕዝቅያስን መጐብኘታቸው፣ ኢሳይያስ ለተናገረው ትንቢት ፍጻሜ ቅድመ ሁኔታን አመቻችቶአል (39፥1:6 እና ማብ ይመ):: የኢየሩሳሌም ውድቀት እስከ 586 ዓ.ቅ.ክ ባይፈጸምም፣ ኢሳይያስ የይሁዳን ውድቀት፣ የሕዝቡን ወደ ባቢሎን ተማርኮ መሄድና ከዚያም በኋላ ከምርኮ ወደ ምድሩ የመመለሳቸውን ተስፋ ተናግሮአል (40፥2-3 እና ማብ ይመ):: እግዚአብሔር ቀደም ሲል ሕዝቡን ከግብፅ አገዛዝ እንደ ታደጋቸው፣ አሁን ደግሞ ከባቢሎን ምርኮ ነጻ ሲያወጣቸው ይታያል (የ35፥9፤ 41፥14 ማብ ይመ):: ከዚህ በኋላ ነቢዩ ኢሳይያስ፣ ፋርስንና ሜዶንን በማዋሐድ በ539 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎንን ስለሚወረው ስለ ፋርሱ ንጉሥ ስለ ቂሮስ መነሣት ይተነብያል (41፥2 እና ማብ ይመ):: በ538 ዓ.ቅ.ክ አይሁድ በነጻነት ወደ አገራቸው መመለስ እንዲችሉ ቂሮስ ያወጣው ዐዋጅ ምቹ ሁኔታን ፈጥሮላቸዋል፤ ይህም ክርስቶስ ሰዎችን ከኀጢአት ነጻ አውጥቶ ታላቅ ድነት እንደሚሰጣቸው የሚያመላክት ነው (52፥7 እና ማብ ይመ)::

### የመጽሐፉ መሪ ሐሳብና ትምህርተ መለኮት

ትንቢተ ኢሳይያስ የእግዚአብሔርን ፍርድና ማዳን ሙሉ ገጽታ ገልጦ የሚያሳይ ነው:: እግዚአብሔር፣ "የእስራኤል ቅዱስ" ተብሎአል (1፥4፤ 6፥1 እና ማብ ይመ)፤ እርሱም ዐመፀኛ የሆነውን ሕዝቡን ይቀጣል (1፥2)፤ የኋላ ኋላ ግን ይቤዣቸዋል (41፥14:16):: እስራኤል የታወረና የደነቈረ ሕዝብ ነው (6፥9-10፤ 42፥7)፤ በማንም የሚረገጥ የወይን ተክል ስፍራ ሆኖአል (5፥1-7)፤ ፍርድና ፍትሕ ተለይቶታል (5፥7፤ 10፥1-2):: በእስራኤልና ለእግዚአብሔር በማይታዘዙ መንግሥታት ሁሉ ላይ የሚመጣው አስፈሪ ፍርድ፣ "የጌታ ቀን" ተብሎአል:: እስራኤል የዚያን ቀን ምንነት ከብዙ በጥቂቱ በሕይወቷ ቀምሳለች (5፥30፤ 42፥25)፤ ሌሎች መንግሥታት ግን ሙሉውን ፍርድ ይቀበላሉ (2፥11:17:20 እና ማብ ይመ):: ይህ ቀን በአዲስ ኪዳን ከጌታ ዳግም ምጽአት እንዲሁም ተከትሎት ከሚመጣው ፍርድ ጋር የተያያዘ ነው (24፥1:21፤ 34፥1-2 እና ማብ ይመ):: በመጽሐፉ ውስጥ ስለ ፍርድ የተጠቀሰው ቍጥር "እሳት" እየተባለ ነው (1፥31፤ 30፥33 እና ማብ ይመ):: እግዚአብሔር ከመንግሥታትና ከነገሥታት ሁሉ እጅግ የሚልቅ ጌታ ነው (የ25፥8 ማብ ይመ፤ በተጨማሪ 40፥15-24 ይመ)::

ያም ሆኖ እግዚአብሔር የሚራራ ነው (14፥1-2)፤ ከፖለቲካና ከመንፈሳዊ ተጽዕኖም ይታደጋቸዋል:: ወደ አገራቸው መመለሳቸውና እንደ ገና መቋቋማቸው እንደ አዲስ ፀአት (መፍለስ) የሚቈጠር ነው (43፥2:16-19፤52፥10-12)፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር ይቤዣቸዋል (35፥9፤ 41፥14 እና ማብ ይመ)፤ ያድናቸዋልም (43፥3፤ 49፥8 እና ማብ ይመ):: የእስራኤል ኀያል ፈጣሪ (40፥21-22፤ 48፥13) በቸርነቱ ወደ ገዛ ምድራቸው በሚመልሳቸው ጊዜ፣ የውሃ ምንጭ በበረሓ ውስጥ እንዲፈልቅ ያደርጋል (32፥2):: በሁለቱም የመጽሐፉ ዋነኛ ክፍሎች ውስጥ ስለ እስራኤል መመለስ በሚያወሣበት ጊዜ፣ አውራ ጐዳና የሚለው ሐረግ ጕልሕ የሆነ መሪ ሐሳብ ነው (11፥16፤ 40፥3 እና ማብ ይመ):: እስራኤል ወደ ምድሯ እንድትመለስ ይለቋት ዘንድ እግዚአብሔር ሰንደቅ ዐላማን ወደ ላይ አንሥቶ ለአሕዛብ መንግሥታት ጥሪ ያደርግላቸዋል (5፥26 እና ማብ ይመ)::

ሰላምና ደኅንነት የዚህ የአዲሱ መስሓዊ ዘመን መለያ ምልክቶች ናቸው (11፥6-9):: ከዳዊት ዘር የተገኘ ንጉሥ ምድሪቱን በጽድቅ ይገዛል (9፥7፤ 32፥1)፤ ሕዝቦችም ሁሉ ወደ ተቀደሰው የኢየሩሳሌም ተራራ ይጐርፋሉ (2፥2-4 እና ማብ ይመ):: የእግዚአብሔር ሕዝብ ከእንግዲህ ወዲህ በክፉ ገዦች አይጨቈኑም (11፥14፤ 45፥14)፤ ኢየሩሳሌምም በእውነት፣ "የእግዚአብሔር ከተማ" ትሆናለች (60፥14)::

ንጉሥ የሆነውን መሲሕ እግዚአብሔር በም 42-53 ባለው ክፍል፣ "አገልጋዬ" ይለዋል፤ እስራኤልም እንደ አንድ ሕዝብ በዚሁ ስያሜ ተጠርታለች (41፥8-9፤ 42፥1 እና ማብ ይመ):: ድነትም ሙሉ በሙሉ ሊገኝ የሚችለው በዚሁ በአገልጋዩ ሥቃይ አማካይነት ነው:: እስራኤልን ከባቢሎን ቀንበር ለማላቀቅ ንጉሡ ቂሮስ የእግዚአብሔር መሣሪያ ነው (41፥2)፤ ክርስቶስ ግን የሰውን ዘር ሁሉ ከኀጢአት እስራት ነጻ አወጣ (52፥13-53፥12):: እርሱም፣ "ለአሕዛብ ብርሃን" ሆነ (42፥6)፤ ከዚህም የተነሣ ፍርድ የሚጠብቃቸው ሕዝቦች (ም 13-23) ድነት ያገኛሉ (55፥4-5):: እነዚህ አሕዛብም፣ "የእግዚአብሔር አገልጋዮች"

ይሆናሉ (54፥17 እና ማብ ይመ)።

የኢሳይያስ መጽሐፍ ዐላማ አድርጎና ቀጥ ብሎ የሚጓዘው፣ በምድር ላይ ወደምትመሠረተውና ገዢም ሕዝቧም ጻድቅ ወደ ሆኑት ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ነው። የታደሰችው ምድርና የታደሰውም ሕዝብ ፍጹም ታዛዥ በመሆን ለመለኮታዊ ዕቅድ ይገዛሉ፤ የዚህም ሁሉ ውጤት የእስራኤል ቅዱስ ላከናወነው ነገር ምስጋናንና ክብርን ለእርሱ ማቅረብ ይሆናል።

## ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያት

የትንቢተ ኢሳይያስ ሥነ ጽሑፍ ስድ ንባብንና ግጥምን የሚያጠቃልል ነው፣ የቅኔው ውበት በብሉይ ተወዳዳሪ አይገኝለትም። ዋናው ስድ ንባብ የሚገኘው ከምዕራፍ 36-39 ባለው ውስጥ ነው፤ ይህም የመጽሐፉን ሁለት ዐበይት ክፍሎች የሚያገናኝ ታሪካዊ መሸጋገሪያ ነው። የቅኔው ክፍል ከም 13-23 ያለውን ተከታታይ ክፍል ያጠቃልላል። የባቢሎንን ንጉሥ ውድቀት በማሳየት የተጻፈው ቅኔ በ14፥4-23 ላይ ይገኛል። በም24-27 ላይ ያለው ክፍል በመጨረሻ ዘመን ላይ የሚያተኵር ራእይ ነክ ትንቢት ነው (የ24፥1 ማብ ይመ)። ስለ ጥበብ የተነገረው ቅኔ በ28፥23-29፤ ላይ ይገኛል (ከ32፥5-8 ጋር ያነጻጽሩ)። የወይን ተክልን ቦታ አስመልክቶ የተዘመረው ግጥምም በ5፥1-7 ላይ ሲገኝ፣ ኢሳይያስ በእግዚአብሔርና በእስራኤል መካከል ያለውን ግንኙነት ለመግለጽ አጀማመሩን የፍቅር ግጥም ዐይነት አድርጎ አቅርቦታል። የምስጋና መዝሙሮች በ12፥1-6 እና በ38፥10-20 ላይ ይገኛሉ፣ ብሔራዊ የሐዘን እንጕርጕሮን የሚገልጽ ቅኔ ደግሞ ከ63፥7-64፥12 ባለው ክፍል ይገኛል። ነቢዩ የተለያዩ ብዙ ቃላት እንደ መጠቀሙ ሁሉ፣ ሥነ ግጥሙም የተዋጣለትና ልዩ ልዩ አቀራረብ ያለው ነው፤ ማንኛውም የብሉይ ኪዳን ጸሐፊ ከጠቀሰው በላይ፣ ከ2200 የሚበልጡ የተለያዩ የዕብራይስጥ ቃላትን ነቢዩ ኢሳይያስ ተጠቅሞአል።

ኢሳይያስ ሕይወት የሌላቸውን ነገሮች ሁኔታ ለመግለጽ በአብዛኛው የተጠቀመበት ሥነ ጽሑፋዊ ዘይቤ ሰውኛ አገላለጽ ነው። ፀሐይና ጨረቃ ሲያፍሩ (24፥23)፣ ምድረ በዳውና ደረቁ ምድር ሐሤት ያደርጋሉ (35፥1 እና ማብ ይመ)፤ ተራሮችና ደኖች ይዘምራሉ (44፥23)፤ ዛፎችም ያጨበጭባሉ (55፥12)። በኢሳይያስ መጽሐፍ ውስጥ ተወዳጅ የሆነው ዘይቤያዊ አገላለጽ የወይኑ ተክል ቦታ ሲሆን፣ የሚወክለውም እስራኤልን ነው (5፥7)። የወይኑ መጭመቂሚያ ቦታ መረገጥ ፍርድን ያመለክታል (51፥17 እና ማብ ይመ)፤ የእግዚአብሔርን የቍጣ ጽዋ መጠጣት በቅጣት ሥር መማቀቅን የሚገልጽ ዘይቤ ነው (51፥17 እና ማብ ይመ)። ኢሳይያስ፣ "ዐምባ"፣ "ዐለት" ወይም "ድንጋይ" የሚለውን ስም እግዚአብሔርን ለመግለጽ ተጠቅሞበታል (17፥10)። ሌዋታንንና ረዓብን የመሳሰሉት እንስሶች ደግሞ የአሕዛብን መንግሥታት የሚገልጹ ናቸው (27፥1፤ 30፥7፤ 51፥9 ይመ)።

የኢሳይያስ ዘይቤያዊ የአገላለጽ ችሎታ በ30፥27-33 ላይ ጐልቶ ይታያል፤ በ44፥9ጠ20 ላይ ደግሞ የጣዖት አምልኮን ለማውገዝ ነቢዩ ሙሉ በሙሉ በሽሙጥ አነጋገር ተጠቅሞአል። በአንድ ተመሳሳይ ንባብ ሁለት ትርጕም ያዘሉ ቃላትን የመጠቀሙ ጕልሕ ምሳሌ በ5፥7 ላይ ይታያል (የዚያኑ ማብ ይመ? በ6፥10 ላይ ደግሞ ተጓዳኝ የሚሆኑ ሐሳቦች ከላይ ወደ ታችና ከታች ወደ ላይ እየተገናኙ የሚሄዱበት አቀራረብ (ኪያስቲክ ውቅር) ይታያል (የዚያኑ ማብ ይመ፤ በጨማሪም የ16፥7 ማብ ይመ)። በተመሳሳይ ፊደል ወይም ድምፅ የሚጀምሩ ቃላትን ወይም በከፊል ተመሳሳይ ድምፀት የሚነበቡ ቃላትን የመጠቀም ዘይቤ (በዕብራይስጡ መጽሐፍ) በ24፥17 ላይ ይገኛል (የዚያኑ ማብ ይመ)። በ28፥15፡18 ላይ ውሑድ ተለዋጭ ዘይቤያዊ አጻጻፍ፣ "ታላቅ መቅሠፍት" በሚለው አገላለጽ ውስጥ ይታያል።

ኢሳይያስ ብዙውን ጊዜ፣ ቀደም ሲል የነበረውን የእስራኤል ታሪክ በተለይ በዘፀአት መጽሐፍ ውስጥ የሚገኘውን በሰያፍ ጠቀስ ያደርጋል። እስራኤላውያን ቀይ ባሕርን የመሻገራቸውን ታሪክ በ11፥5 እና 43፥2፡16-17 ላይ ላለው ሐሳብ መሠረት አድርጎአል፤ ደግሞም በ4፥5-6፤ 31፥5፤ 37፥36 ላይ ከቀድሞ የብሉይ ኪዳን ታሪክ ጠቀስ የተደረጉ ሐሳቦች አሉ (የእነዚህን ጥቅሶች ማብ ይመ)። የሰዶምና የገሞራ መደምሰስ በ1፥9 ላይ ተጠቅሶአል፤ ጌዴዎን በምድያም ሰዎች ላይ ያገኘው ድል በ9፥4፤ 10፥26 ላይ ተመልክቶአል (በተጨማሪ 28፥21 ይመ)። ኢሳይያስ በዘዳ 32 ላይ የሚገኘውን የሙሴን መዝሙር ብዙ ጊዜ ጠቃቅሶት እናገኛለን (1፥2 እና ዘዳ 32፥1፤ 30፥17፤ እና ዘዳ 32፥30፤ 43፥11፡13፤ 32፥39 ያነጻጽሩ)። ሙሴ እንዳደረገው ሁሉ፣ ኢሳይያስም ሕዝቡ ንስሐ እንዲገባና ሁሉን ቻይ በሆነው በቅዱስ እግዚአብሔር እንዲያምን ጥሪ ያቀርባል። በተጨማሪ የ49፥8ን ማብራሪያ ይመልከቱ።

## አስተዋፅኦ

### ክፍል አንድ፤ የፍርድ መጽሐፍ (ም 1-39)

1. የተግሣጽና የተስፋ መልእክቶች (ም 1-6)
   - ሀ. መግቢያ፤ ይሁዳ ቃል ኪዳን በማፍረሷ የቀረበባት ክስ (ም 1)
   - ለ. በይሁዳና በኢየሩሳሌም ላይ ወደ ፊት የሚመጣው ቅጣትና የሚያገኙት ክብር (ም 2-4)
     - (1) የኢየሩሳሌም የወደፊት በረከቶች (2፥1-5)
     - (2) እግዚአብሔር ይሁዳን መቅጣቱ (2፥6-4፥1)
     - (3) የጽዮን እንደ ገና መታደስ (4፥2-6)
   - ሐ. በሕዝቡ ላይ የሚፈጸመው ፍርድና በምርኮ መወሰዳቸው (ም 5)
   - መ. የኢሳይያስ ልዩ ጥሪና ተልእኮ (ም 6)

2. ሶርያና እስራኤል ይሁዳን ለማጥቃት በመተባበራቸው የተነገረ ትንቢት (ም 7-12)
   - ሀ. አካዝ ሶርያና እስራኤል በመተባበራቸው እንዳይፈራ የተሰጠው ማስጠንቀቂያ (ም 7)
   - ለ. የኢሳይያስ ልጅና የዳዊት ልጅ (8፥1-9፥7)
   - ሐ. በእስራኤል ላይ የተነገረ ፍርድ (9፥8-10፥4)
   - መ. የአሦር ግዛትና የዳዊት መንግሥት (10፥5-12፥6)
     - (1) የአሦር መደምሰስ (10፥5-34)
     - (2) ከዳዊት ዘር የሆነ ንጉሥ መንገሡና የዳዊትን መንግሥት መመሥረቱ (ም 11)
     - (3) ነጻ ስለ ወጡ የተዘመረ የደስታ መዝሙር (ም 12)
3. በአሕዛብ መንግሥታት ላይ የተነገረ ፍርድ (ም 13-23)
   - ሀ. በአሦርና በባቢሎን ላይ (13፥1-14፥27)
   - ለ. በፍልስጥኤም ላይ (14፥28-32)
   - ሐ. በሞዓብ ላይ (ም 15-16)
   - መ. በሶርያና በእስራኤል ላይ (ም 17)
   - ሠ. በኢትዮጵያ ላይ (ም 18)
   - ረ. በግብፅና በኢትዮጵያ ላይ (ም 19-20)
   - ሰ. በባቢሎን ላይ (21፥1-10)
   - ሸ. በኤዶም ላይ (21፥11-12)
   - ቀ. በዐረብ ላይ (21፥13-17)
   - በ. በራእይ ሸለቆ (በኢየሩሳሌም) ላይ (ም 22)
   - ተ. በጢሮስ ላይ (ም23)
4. ፍርድና ተስፋ (የእግዚአብሔር መንግሥት) (ም24-27)
   - ሀ. ፍጥረት ሁሉ ለፈጸመው ኀጢአት ሁለንታዊ ፍርድ (ም 24)
   - ለ. ነጻ መውጣትና በረከት (ም 25)
   - ሐ. እግዚአብሔር ላደረገው መለኮታዊ ክብካቤ የቀረበ ምስጋና (ም 26)
   - መ. የእስራኤል ትሩፋን እንደ ገና መመለስና የጠላቶቻቸው መቀጣት (ም 27)
5. ስድስት ወዮታዎች፤ አምስቱ በእስራኤል ላሉ ከዳተኞች፤ አንዱ በአሦር ላይ (ም 28-33)
   - ሀ. ወዮ ለኤፍሬም (ለሰማርያ) እንዲሁም ለይሁዳ (ም 28)
   - ለ. ወዮ ለዳዊት ከተማ ለኢየሩሳሌም (29፥1-14)
   - ሐ. ወዮ በባዕዳን አጋርነት ለሚታመኑ (29፥15-24)
   - መ. ወዮ ለእልከኛ ሕዝብ (ም 30)
   - ሠ. ወዮ በግብፅ ለሚታመኑ (ም 31-32)
   - ረ. ወዮ ለአሦር፤ በረከት ግን ለእግዚአብሔር ሕዝብ (ም 33)
6. ተጨማሪ የፍርድና የተስፋ ትንቢቶች (ም 34-35)
   - ሀ. የአሕዛብ መደምሰስና ለእግዚአብሔር ሕዝብ የተደረገ የበቀል እርምጃ (ም 34)
   - ለ. እንደ ገና ለታደሰችው፣ ለጽዮን የተነገረ የበረከት ተስፋ (ም 35)
7. ከአሦራውያን ዛቻ ወደ ባቢሎን ምርኮ የመሄድ ታሪካዊ ሽግግር (36-39)
   - ሀ. ኢየሩሳሌም ከአሦራውያን ዛቻ መጠበቋ (ም 36-37)
     - (1) ኢየሩሳሌም በሰናክሬምና በአሦራውያን ሰራዊት መከበቧ (ም 36)
     - (2) እግዚአብሔር ኢየሩሳሌምን መታደጉ (ም 37)
   - ለ. እግዚአብሔር የሕዝቅያስን ዕድሜ ማርዘሙ (ም 38)
   - ሐ. ወደ ባቢሎን ተማርኮ ስለመሄድ አስቀድሞ መነገሩ (ም 39)

**ክፍል ሁለት፤ የመጽናናት መጽሐፍ (ም 40-66)**

8. የእስራኤል ነጻ መውጣትና እንደ ገና መደርጀት (ም 40-48)
   - ሀ. የድል አድራጊው እግዚአብሔር መምጣት (40፥1-26)
   - ለ. ተስፋ ቈርጠው የዛሉትን ምርኮኞች የሚያበረታ ጽኑ ኀይል (40፥27-31)
   - ሐ. እግዚአሔር የታሪክ ጌታ (41፥1-42፥9)
   - መ. ምስጋናና ምክር (42፥10-25)
   - ሠ. የእስራኤል እንደ ገና መሰባሰብና መታደስ (43፥1-44፥5)
   - ረ. ወደር የሌለው ብቸኛ አምላክ (44፥6-45፥25)
   - ሰ. ከባቢሎን አማልክት ይልቅ እግዚአብሔር ኀያል መሆኑ (ም 46)

ሸ. የባቢሎን አወዳደቅ (ም 47)
ቀ. እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሰጠው ጥብቅ ምክር (ም 48)

9. የእግዚአብሔር ባሪያ ተልእኮና የእስራኤል መታደስ (ም 49-57)

ሀ. የእግዚአብሔር ባሪያ መጠራትና ተልእኮው (49፥1-13)
ለ. ጽዮን እንደ ገና ሕዝብ በሕዝብ መሆኗ (49፥14-26)
ሐ. የእስራኤል ኀጢአትና የእግዚአብሔር ባሪያ መታዘዝ (ም 50)
መ. ቅሬታዎች ወደ ፊት ከሚጠብቃቸው ታላቅ ክብር የተነሣ መጽናናታቸው (51፥1-52፥12)
ሠ. የጌታ ጻድቅ ባሪያ የሚደርስበት መከራና የሚያገኘው ክብር (52፥13-53፥12)
ረ. የጽዮን የወደ ፊት ክብር (ም 54)
ሰ. እግዚአብሔር ለድነትና ለቃል ኪዳኑ በረከት መጥራቱ (55፥1-56፥8)
ሸ. በእስራኤል ባሉ ክፉዎች ላይ መፈረዱ (56፥9-57፥21)

10. ዘላለማዊ ትድግናና ዘላለማዊ ፍርድ (ም 58-66)

ሀ. ሐሰተኛና እውነተኛ አምልኮ (ም 58)
ለ. የጽዮን ኑዛዜና የምታገኘው ቤዛ (ም 59)
ሐ. የጽዮን ሰላምና ብልጥግና (ም 60)
መ. እግዚአብሔር የሚወደው (ም 61)
ሠ. የጽዮን መታደስና ክብር (62፥1-63፥6)
ረ. እግዚአብሔር ሕዝቡን እንዲታደግ የተደረገ ጸሎት (63፥7-64፥12)
ሰ. የእግዚአብሔር መልስ፤ ምሕረትና ፍርድ (ም 65)
ሸ. በሐሰት በሚያመልኩት ላይ የሚመጣ ፍርድና በእውነት ለሚያመልኩት የሚወርድ በረከት (ም 66)

**1** በይሁዳ ነገሥታት በዖዝያን፣ በኢዮአታም፣ በአካዝና በሕዝቅያስ ዘመን፣ የአሞጽ ልጅ ኢሳይያስ ስለ ይሁዳና ስለ ኢየሩሳሌም ያየው ራእይ፤

## እምቢተኛ ሕዝብ

[2]ሰማያት ሆይ፤ ስሙ! ምድር ሆይ፤ አድምጪ!
*እግዚአብሔር* እንዲህ ሲል ተናግሮአልና፤
"ልጆች ወለድሁ፣ አሳደግኋቸውም፤
እነርሱ ግን ዐመፁብኝ።
[3]በሬ ጌታውን፣
አህያ የባለቤቱን ጋጥ ያውቃል፤
እስራኤል ግን አላወቀም፤
ሕዝቤም አላስተዋለም።"

[4]እናንተ ኀጢአተኛ ሕዝብ፣
በደል የሞላበት ወገን፣
የክፉ አድራጊ ዘር፣
ምግባረ ብልሹ ልጆች ወዮላችሁ!
*እግዚአብሔርን* ትተዋል፤
የእስራኤልን ቅዱስ አቃለዋል፤
ጀርባቸውንም በእርሱ ላይ አዙረዋል።

[5]ለምን ዳግመኛ ትመታላችሁ?
ለምንስ በዐመፅ ትጸናላችሁ?
ራሳችሁ በሙሉ ታሞአል፤
ልባችሁ ሁሉ ታውኮአል።
[6]ከእግር ጥፍራችሁ እስከ ራስ ጠጕራችሁ
ጤና የላችሁም፤
ቍስልና ዕባጭ እንዲሁም እዥ ብቻ ነው፤
አልታጠበም፤ አልታሰረም፤
በዘይትም አልለዘበም።

[7]አገራችሁ ባድማ፣
ከተሞቻችሁ በእሳት የተቃጠሉ ይሆናሉ፤
ዕርሻችሁ እያየ፣
መሬታችሁ በባዕድ ይነጠቃል፤
ጠፍም ይሆናል።
[8]የጽዮን ሴት ልጅ
በወይን እትክልት ውስጥ እንዳለ ዳስ፣
በዱባ ተክል ወስጥ እንደሚገኝ ጐጆ፣
እንደ ተከበበም ከተማ ተተወች።
[9]የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር*
ዘርን ባያስቀርልን ኖሮ፣
እንደ ሰዶም በሆንን
ገሞራንም በመሰልን ነበር።

[10]እናንተ የሰዶም ገዦች፤
የ*እግዚአብሔርን* ቃል ስሙ፤
እናንተ የገሞራ ሰዎች፤
የ*እግዚአብሔርን* ሕግ አድምጡ።
[11]"የመሥዋዕታችሁ ብዛት
ለእኔ ምኔ ነው?" ይላል *እግዚአብሔር*።
"የሚቃጠለውን የአውራ በግና
የሰቡ እንስሳትን ስብ ጠግቤአለሁ፤
በበሬ፣ በበግ ጠቦትና በፍየል ደም ደስ
አልሰኝም።
[12]በፊቴ ለመቅረብ ስትመጡ፣
ይህን ሁሉ እንድታመጡ፣
የመቅደሴን ደጅ እንድትረግጡ ማን
ጠየቃችሁ?
[13]ከንቱውን መባ አታቅርቡ፤
ዕጣናችሁን እጸየፋለሁ፤
የወር መባቻ በዓላችሁን፣

1፥1 1ሳሙ3፥1፤ 2ነገ14፥21፤16፥1፤ 1ዜና3፥12፡13፤ 2ዜና26፥22፤ነህ1፥1፤ ኢሳ2፥1፤13፥1፤22፥1፡ 5፤40፥9፤44፥26፤ አብ1፥1፤ናሆ1፥1
1፥2 ቍ4:23፤ ዘዳ4፥26፤መሳ11፥10፤ ኢሳ23፥4፤24፥5:20፤ 30፥1:9፤46፥8፤ 48፥8፤57፥4፤63፥16፤ 65፥2፤66፥24፤ ኤር42፥5፤ሕዝ24፥3፤ ሚክ1፥2፤ሐጌ1፥12፤ ሚል1፥6፤3፥5
1፥3 ዘፍ42፥27፤ ዘዳ32፥28፤ኢዮ12፥9፤ ኢሳ42፥25፤48፥8፤ ኤር4፥22፤5፥4፤9፥3፡ 6፤ሆሴ2፥8፤4፥1:6፤ 7፥9
1፥4 ቍ2፤ዘዳ32፥15፤ 2ነገ19፥22፤ መዝ14፥3፤119፥87፤ ምሳ30፥9፤ኢሳ5፥18፡ 19:24፤9፥17፤14፥20፤ 31፥1:2፤37፥23፤ 41፥14፤43፥14፤45፥11፤ 47፥4፤59፥13፤ ኤር23፥14፤ሕዝ39፥7
1፥5 ቍ2፤ ምሳ20፥30፤ ኢሳ30፥26፤ 31፥6፤33፥6:24፤ 58፥8፤ኤር2፥30፤ 5፥3፤8፥5፤30፥17፤ 44፥16-17፤ሰቆ2፥11፤ 5፥17፤ዕብ3፥16
1፥6 ዘዳ28፥35፤ 2ሳሙ14፥2፤መዝ23፥5፤ 38፥3፤45፥7፤104፥15፤ 147፥3፤ኢሳ30፥26፤ 53፥5፤61፥3፤ኤር8፥22፤ 14፥19፤30፥17፤ ሰቆ2፥13፤ሕዝ34፥4፤ ሉቃ10፥34
1፥7 ዘሌ26፥16:31:34፤ ዘዳ29፥23፤ መሳ6፥3-6፤2ነገ18፥13፤መዝ109፥11፤ኢሳ62፥8፤ኤር5፥17
1፥8 ኢዮ27፥18፤መዝ9፥14፤ኢሳ10፥32፤30፥17፤49፥21
1፥9 ዘፍ19፥24፤45፥7፤2ነገ21፥14፤ኢሳ4፥2፤6፥13፤27፥12፤28፥5፤ 37፥4:31-32፤45፥25፤56፥8፤ኤር23፥3፤ ኢል2፥32፤ሮሜ9፥29
1፥10 ዘፍ13፥13፤18፥20፤ኢሳ5፥24፤8፥20፤13፥19፤28፥14፤30፥9፤ ሕዝ16፥49፤ሮሜ9፥29፤ራእ11፥8 1፥11 1ሳሙ15፥22፤ኢዮ22፥3፤ መዝ40፥6፤50፥8፤ኢሳ66፥3፤ ኤር6፥20፤አሞ6፥4፤ሚል1፥10፤ዕብ10፥4
1፥12 ዘፀ23፥17፤ ዘዳ31፥11 1፥13 ዘኁ10፥10፤1ነገ14፥24፤ 1ዜና23፥31፤መዝ115፥8፤ ምሳ15፥8፤28፥9፤ኢሳ41፥24፤66፥3፤ ኤር7፥9፤18፥15፤44፥8፤ሐጌ2፥14፤ሚል2፥11

*1፥1-31፤* በምዕራፍ 1 እና በምዕራፍ 5 ላይ የተጻፉትን ወቀሳዎች ያነጻጽሩ፤ ሁለቱም ምዕራፎች የመጀመሪያዎቹን ሁለት ትንቢቶች ያጠቃልላሉ። በተለይ ምዕራፍ አንድ ለመጽሐፉ መግቢያ ሆኖ ይቈጠራል።

*1፥1፤ በዖዝያን፣ በኢዮአታም፣ በአካዝና በሕዝቅያስ፤* እነዚህ ነገሥታት የገዙት ከ792 እስከ 686 ዓ.ቅ.ክ ነው። የሰሜኑ የእስራኤል ነገሥታት ስም ያልተጠቀሰው፣ ኢሳይያስ ያገለገለው በደቡቡ መንግሥት በይሁዳ ብቻ ስለ ሆነ ነው። የመጽሐፉ ርእስ ነው። ሌሎችም ርእሶች ላይ ተገልጾአል በ2፥1፤ 13፥1፤ 14፥28፤ 15፥1፤ 17፥1፤ 19፥1፤ 21፥1:11:13፤ 22፥1፤ 23፥1። *የአሞጽ፤* ከነቢዩ አሞጽ ጋር አንድ አይደለም። *ራእይ፤* መገለጥን ወይም ትንቢትን በተመለከተ 1ሳሙ 3፥1፤ ምሳ 29፥18፤ አብ 1 ይመ።

*1፥2፤* ኢሳይያስ ትንቢቱን የሚጀምረውም፣ የሚጨርሰውም (66፥24) በእግዚአብሔር ላይ ያመፁትን በመቃወም ነው። ነቢዩ ኢሳይያስ፣ የእስራኤል ሕዝብ የቃል ኪዳኑ ምስክር በመሆናቸው (ዘዳ 30፥19፤ 31፥28፤ 32፥1)፣ እግዚአብሔር በእነርሱ ላይ የሚያስማው ክስ ተገቢ መሆኑንና የፍርዱንም ትክክለኛነት ለማሳየት ሰማይንና ምድርን ምስክር አድርጎ ይጠራቸዋል።

1፥3 *ጋጥ፤* ከብቶች የሚያድሩበት ማጕሪያ ወይም የሚበሉበትና የሚጠጡበት ገንዳ። እግዚአብሔርን ለማወቅና የበለጠ ለመረዳት አለመፈለግ፣ በኋላ ይሁዳ ከምድሯ ተነቅላ እንድትሄድ ምክንያት ሆነ (5፥13)።

1፥4 *የእስራኤልን ቅዱስ፤* በኢሳይያስ መጽሐፍ 26 ጊዜ ተጠቅሶአል (በተለይ 5፥24 ይመ)፤ በሌሎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ላይ ተጠቅሶ የምናገኘው 6 ጊዜ ብቻ ነው።

*1፥5-6፤* አሳዛኝ የሆነው የእስራኤል ሕዝብ የግብረገብና የመንፈሳዊ ድቀት ክሥተት በኢሳይያስ 53፥4-5 እንደ ተገለጠው መከራን በገዛ ፈቃዱ ወደ ተቀበለው አገልጋይ ተዛውሮአል።

*1፥6፤* እንደ ኢዮብ ቍስል ሁሉ መላውን አካል ያዳረሰ ማለት ነው (ኢዮ 2፥7)። *ዘይት፤* ቍስልን ለማከም የታወቀ መድኀኒት ነው (ሉቃ 10፥34)።

*1፥7-9፤* የይሁዳ ምድር ጠፍ የሆነው፣ በውጭ ኀይሎች ወረራ ምክንያት ነበር፣ ለምሳሌ ሰሜኑ የእስራኤል መንግሥት፣ ኤዶምና ፍልስጥኤም ወረውት ነበር (2ዜና 28፥5-18)፤ ቀጥሎም በ701 ዓ.ቅ.ክ ላይ ንጉሥ ሰናክሬምና የአሦር ሰራዊት ወረሩት (36፥1-2)፤ ከዚያም በኋላ ማለት ከ605-586 ዓ.ቅ.ክ ባለው ጊዜ ንጉሥ ናቡከደነፆርና የአዲሲቱ ባቢሎን ሰራዊት አገሩን በሙሉ ያዙ።

1፥8 *የጽዮን ሴት ልጅ፤* ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን የሚያመለክት ነው። *ዳስ … ጐጆ፤* ሌቦችንና ቀማኞችን፣ ነቅተው የሚጠብቁ ሰዎች (ኢዮ 27፥18) የሚጠቀሙባቸው ጊዜያዊ መጠለያዎች ናቸው። ስለዚህ ኢየሩሳሌም የተጠናከረ መከላከያ አልነበራትም ማለት ነው።

1፥9-10 *ሰዶም … ገሞራንም፤* በኀጢአታቸው ምክንያት ፈጽሞ ለጠፉ ከተሞች ምሳሌ በመሆን ከጥንት ጀምሮ የሚጠቀሱ ቦታዎች ናቸው (3፥9፤ ዘፍ 13፥13፤ 18፥20-21:19፥5:24-25 ይመ)። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ጴጥሮስን፣ "አንተ ሰይጣን" (ማቴ 16፥23) እንዳለው ሁሉ፣ ኢሳይያስም የአገሩን ሰዎች የሰዶም ገዦችና የገሞራ ሰዎች ይላቸዋል።

*1፥9፤* ከኢሳ 10፥22-23 ጋር ተያይዞ በሮሜ 9፥29 ላይ ተጠቅሷል። እግዚአብሔር ከሚያመጣው ፍርድ ተርፈው ርስት የሚወርሱትን ቅሬታዎች ያመለክታል (4፥3፤ 10፥20-23፤ 11፥11:16፤ 46፥3 ይመ)።

*1፥11-15፤* እጅግ በጣም አስፈላጊው ነገር፣ የሚያመልከው ሰው የሚፈጽማቸው የተለያዩ ሃይማኖታዊ ድርጊቶች ሳይሆኑ፣ ራሱ ሰውየው በእውነት እግዚአብሔርን ያመልካል ወይ? የሚለው ነው (66፥3፤ ኤር 7፥21-26፤ ሆሴ 6፥6፤ አሞ 5፥21-24፤ ሚክ 6፥6-8 ይመ)።

1፥11 *የሰቡ እንስሳትን፤* የሚያሰባና የሚያወፍር ልዩ ምግብ

ሰንበቶቻችሁን፣ ጉባኤያችሁንና
በክፋት የተሞላውን ስብሰባችሁን መታገሥ
  አልቻልሁም።
[14]የወር መባቻችሁንና የተደነገጉ በዓሎቻችሁን
  ነፍሴ ጠልታለች፤
ሸክም ሆነውብኛል፤
  መታገሥም አልቻልሁም።
[15]እጆቻችሁን ለጸሎት ወደ እኔ ስትዘረጉ፣
  ዐይኖቼን ከእናንተ እሰውራለሁ፤
አብዝታችሁ ብትጸልዩም እንኳ አልሰማችሁም፤
  እጆቻችሁ በደም ተበክለዋል፤
[16]ታጠቡ፤ ራሳችሁንም አንጹ፤
  ክፉ ሥራችሁን
ከፊቴ አርቁ፤
  ክፉ ማድረጋችሁን ተዉ፤
[17]መልካም ማድረግን ተማሩ፤
  ፍትሕን እሹ፣
የተገፉትን አጽናኑ[υ]፤
  አባት ለሌላቸው ቁሙላቸው፤
  ለመበለቶችም ተሟገቱ።
[18]"ኑና፤ እንዋቀስ"
  ይላል እግዚአብሔር፤
"ኀጢአታችሁ እንደ ዐለላ ቢቀላ
  እንደ በረዶ ይነጣል፤
እንደ ደም ቢቀላም
  እንደ ባዘቶ ነጭ ይሆናል።
[19]እሺ ብትሉ፣ ብትታዘዙም
  የምድርን በረከት ትበላላችሁ፤
[20]እምቢ ብላችሁ ብታምፁ ግን
  ሰይፍ ይበላችኋል።"
የእግዚአብሔር አፍ ይህን ተናግሮአልና።
[21]ታማኝ የነበረችው ከተማ
  እንዴት አመንዝራ እንደ ሆነች ተመልከቱ!
ቀድሞ ፍትሕ የሞላባት፣
  ጽድቅ የሰፈነባት ነበረች፤
  አሁን ግን የነፍሰ ገዳዮች ማደሪያ ሆነች!
[22]ብርሽ ዝጎአል፣
  ምርጥ የወይን ጠጅሽ ውሃ ገብቶበታል፤

1፥14 ዘፀ12፥16፤ ዘሌ23፥1-44፤ ዘኍ28፥11-29፡39፤ዘዳ16፥1-17፤ ነህ10፥33፤ኢዮ7፥12፤ መዝ11፥5፤69፥3፤ ኢሳ5፥12፤7፥13፤ 29፥1፤43፥22፡24፤ ኤር44፥22፤ሆሴ2፥11፤ ሚል2፥17፤3፥14
1፥15 ዘፀ9፥29፤ ዘዳ1፥45፤31፥17፤ 1ሳሙ8፥18፤ ኢዮ9፥30፤15፥31፤ ኢሳ4፥4፤57፥17፤ 59፥2፡3፤ኤር2፥34፤ ሕዝ7፥23፤ሆሴ4፥2፤ ኢል3፥21፤ዮሐ9፥31
1፥16 ዘኍ19፥11፡16፤ሩት3፥3፤ ኢሳ52፥11፤55፥7፤ ኤር25፥5፤ ማቴ27፥24፤ያዕ4፥8
1፥17 ቆላ23፤ ዘፀ22፥22፤ዘዳ14፥29፤ ኢዮ22፥9፤መዝ34፥14፤ 72፥1፤82፥3፤94፥6፤ ኢሳ10፥2፤11፥4፤ 33፥5፤56፥1፤61፥8፤ ሕዝ18፥31፤22፥7፤ አሞ5፥14-15፤ ሚክ6፥8፤ሶፎ2፥3፤ ሉቃ18፥3፤ያዕ1፥27
1፥18 1ሳሙ2፥25፤ መዝ51፥7፤ኢሳ41፥1፤ 43፥9፡26፤55፥7፤ ራእ7፥14
1፥19 ዘዳ30፥15-16፤ ዕዝ9፥12፤ኢዮ36፥11፤ መዝ34፥10፤ ኢሳ30፥23፤50፥10፤ 55፥2፤58፥14፤62፥9፤ 65፥13፡21-22
1፥20 ዘኍ23፥19፤ 1ሳሙ12፥15፤ ኢዮ15፥22፤ኢሳ3፥25፤ 21፥17፤27፥1፤34፥16፤ 40፥5፤58፥14፤65፥12፤ 66፥16፤ ኤር17፥27፤49፥13፤ ሚክ4፥4፤ዘካ1፥6፤ ራእ1፥16
1፥21 ምሳ6፥17፤ ኢሳ5፥7፤46፥13፤

[23]ገዦችሽ ዐመፀኞችና
  የሌባ ግብረ ዐበሮች ናቸው፤
ሁሉም ጉቦን ይወዳሉ፤
  እጅ መንሻንም በብርቱ ይፈልጋሉ፤
አባት ለሌላቸው አይቆሙም፤
  የመበለቶችንም አቤቱታ አይሰሙም።
[24]ስለዚህ ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
  የእስራኤል ኀያል እንዲህ ይላል፤
"በባላንጣዎቼ ላይ ቍጣዬን እገልጣለሁ፤
  ጠላቶቼንም እበቀላለሁ።
[25]እጄን በአንቺ ላይ አነሣለሁ፣
  ዝገትሽን ፈጽሜ አጠራለሁ፤
  ጕድፍሽንም ሁሉ አስወግዳለሁ።
[26]ፈራጆችሽን እንደ ጥንቱ፣
  አማካሪዎችሽንም እንደ ቀድሞው እመልሳለሁ፤
ከዚያም የጽድቅ መዲና፣
  የታመነች ከተማ
  ተብለሽ ትጠሪያለሽ።
[27]ጽዮን በፍትሕ፣
  በንስሓ የሚመለሱ ነዋሪዎቿም በጽድቅ
  ይዋጃሉ።
[28]ዐመፀኞችና ኀጢአተኞች ግን በአንድነት
  ይደቃሉ፤
  እግዚአብሔርንም የሚተዉ ይጠፋሉ።
[29]"ደስ በተሰኛችሁባቸው የአድባር ዛፎች
  ታፍራላችሁ፤

57፥3-9፤59፥14፤ኤር2፥20፤3፥2፡9፤13፥27፤ሕዝ23፥3፤ሆሴ2፥1-13፤ አሞ6፥12 1፥22 መዝ119፥119 1፥23 ቆላ2፤ዘፀ3፥8፤ዘዳ19፥14፤ ኢሳ10፥2፤ኤር5፥28፤ሕዝ22፥6-7፤አሞ5፥12፤ሚክ2፥1-2፤3፥9፤ 6፥12፤ዕን1፥4 1፥24 ዘፍ49፥24፤ ዘዳ32፥43፤ኢሳ10፥3፤34፥2፡8፤ 35፥4፤47፥3፤59፥17፤61፥2፤63፥4፤ ኤር51፥6፤ሕዝ5፥13
1፥25 ዘዳ28፥63፤2ዜና29፥15፤መዝ78፥38፤ 119፥119፤ኢሳ48፥10፤ ኤር6፥29፤9፥7፤ሕዝ22፥22፤ሚል3፥3 1፥26 ዘፍ32፥28፤ኢሳ4፥3፤ 32፥16፤33፥5፤46፥13፤48፥2፡18፤52፥1፤60፥14፤61፥11፤62፥1፡2፤ 64፥10፤ኤር31፥23፤ 33፥7፡11፤ዳን9፥24፤ሚክ4፥8፤ዘካ8፥3
1፥27 ኢሳ30፥15፤31፥6፤35፥10፤41፥14፤43፥1፤52፥3፤59፥20፤ 62፥12፤63፥4፤ሕዝ18፥30፤ሆሴ2፥19 1፥28 ዘዳ32፥15፤መዝ9፥5፤ ኢሳ24፥20፤33፥14፤43፥27፤48፥8፤50፥1፤59፥2፤66፥24፤ኤር4፥18፤ 16፥4፤42፥22፤44፥12፤ 2ተሰ1፥8-9 1፥29 መዝ97፥7፤ኢሳ42፥17፤ 44፥9፡11፤ 45፥16፤57፥5፤65፥3፤66፥17፤ኤር10፥14፤ሕዝ6፥13፤ሆሴ4፥13

[υ]17 ወይም፣ *ጨቋኙን ገሥጹ* ማለት ነው።

እንዲያገኙ በታ የተለየላቸው እንስሳት ናቸው።

1፥14 *መባቻችሁንና ... በዓሎቻችሁን፤* ወር በገባ በመጀመሪያው ቀን የሚከበር በዓል ነው። የተለያዩ መሥዋዕቶችና ግብሮቻቸው የበዓሉ ዝግጅት ክፍል ናቸው (ዘኍ 28፥11-15 ይመ)። *የተደነገጉ በዓሎች፤* በየዓመቱ የሚከበሩትን በዓሎች ማለት ፋሲካን፣ ሰንበታትን፣ በዓለ አምሳንና የዳስ በዓልን ይጨምራል ዘፀ 23፥14-17፤ 34፥18-25፤ ዘሌ 23፤ ዘዳ 16፥1-17 ይመ)።

1፥15 *ዐይኖቼን ከእናንተ እሰውራለሁ፤* በ8፥17 እና በ59፥2 እግዚአብሔር ፊቱን ከእስራኤል ይሰውራል (ሚክ 3፥4 ይመ)።

*1፥17፤* ኤር 22፥16፤ ያዕ 1፥27 ይመ። *አባት ለሌላቸው ... ለመበለቶችም፤* ደካማ የሆኑትንና የተጨቈኑትን የኅብረተ ሰብ ክፍሎች ይወክላሉ። ገዦች እነዚህን እንዳይበድሉአቸው ማስጠንቀቂያ ተሰጥቶአቸዋል (ቆላ 23፤ 10፥2፤ ኤር 22፥3 ይመ)።

1፥18 *ዐለላ ... ደም፤* የነፍስ ገዳዮችን እጅ የበከለውን ደም ያመለክታል (ቊ 15፥21 ይመ)። *እንደ በረዶ ይነጣል፤* ይቅርታ ከፍተኛ ውጤት እንዳለው የሚያሳይ ጠንካራ ምሳሌያዊ አገላለጽ ነው (መዝ 51፥7 ይመ)። ይህ የይቅርታ ስጦታ የሚገኘው በቊ 19 ላይ በተደረገው ጥሪ መሠረትና በታዛዥም የሕይወት ለውጥ ሁኔታ ነው።

1፥19-20 *በረከት ትበላላችሁ ... ሰይፍ ይበላችኋል፤* ግልጽ የሆነውን ንጽጽር በአንድ የዕብራይስጥ ግሥ ብቻ በመጠቀም ለማሳየት ተችሎአል።

*1፥21፤* መሳውን ይሁዳ የምትወክለው ኢየሩሳሌም ለእግዚአብሔር ያላትን ታማኝነት ያጐደለች ሚስት ሆና ተገኝታለች። ጣዖታትንና ባዕዳን አማልክትን በመከተሏ በመንፈሳዊ አመለካከት አመንዝራ ሆናለች (ቊ 4፤ ኤር 3፥6-14፤ ሕዝ 16፥25-26 ይመ)።

1፥24 *ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣ የእስራኤል ኀያል፤* የእግዚአብሔር ጻኝነት ሥልጣን ምን ያህል ታላቅ እንደ ሆነ በአጽንዖት ይገልጻል።

1፥25-26 *አነሣለሁ ... እመልሳለሁ፤* በአንዱ የዕብራይስጥ ግሥ ብቻ በመጠቀም ንጽጽሩን በሚገባ ለማሳየት ተችሎአል (የቊ 19-20 ማብ ይመ)።

1፥25 *ዝገትሽን ፈጽሜ አጠራለሁ፤* የሚያጠራ እሳት በ4፥4፤ በ48፥10 ላይም ተጠቅሶአል።

1፥26 *የታመነችም ከተማ፤* ቊ 21 ይመ። ተቀራራቢ ወይም ተዛማጅ በሆነ የዕብራይስጥ ስም በመጠቀም የወደፊቷን ኢየሩሳሌም በዘካ 8፥3፣ "የእውነት ከተማ" ብሎአታል።

*1፥27-28፤* ለጽዮን (ለኢየሩሳሌም) በተደረገላት አጠቃላይ ትድግናና ንስሐ ለመግባት አሻፈረን ባሉት ሰዎች ሞት መካከል የቀረበው ንጽጽር በ65፥8-16 ላይ ተስፋፍቶ ቀርቦአል።

1፥29 *የአድባር ዛፎች ... የአትክልት በታዎች፤* ጣዖትን ለማምለክ እንዲህ ባሉ ስፍራዎች መሥዋዕት ይቀርባል፤ ዝሙትም ይፈጸማል (65፥3፤ 66፥17 ይመ)።

በመረጣችኋቸውም የአትክልት ቦታዎች
ትዋረዳላችሁ::
[30]ቅጠሉ እንደ ጠወለገ ወርካ፣
ውሃም እንደሌለው የአትክልት ቦታ ትሆና
ላችሁ::
[31]ብርቱ ሰው እንደ ገለባ፣
ሥራውም እንደ ብልጭታ ይሆናል፤
ሁለቱም አብረው ይቃጠላሉ፤
እሳቱንም የሚያጠፋው የለም::

*የእግዚአብሔር ተራራ*

**2** የአሞጽ ልጅ ኢሳይያስ ስለ ይሁዳና ስለ ኢየሩሳሌም ያየው ይህ ነው፤
[2]በዘመኑም ፍጻሜ፣
*የእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ተራራ
ከተራሮች ከፍ ብሎ ይመሠረታል፤
ከኰረብቶችም በላይ ከፍ ከፍ ይላል፤
ሕዝቦችም ሁሉ ወደዚያ ይጐርፋሉ::
[3]ብዙ ሕዝቦችም መጥተው እንዲህ ይላሉ፤
"ኑ፤ ወደ *እግዚአብሔር* ተራራ፣
ወደ ያዕቆብ አምላክ ቤት እንውጣ፤
እርሱ መንገዱን ያስተምረናል፤
በጐዳናውም እንሄዳለን::"
ሕግ ከጽዮን፣
*የእግዚአብሔር* ቃል ከኢየሩሳሌም ይወጣልና::
[4]እርሱ በሕዝቦች መካከል ይፈርዳል፤
የብዙ ሰዎችን አለመግባባት ያስወግዳል::
እነርሱም ሰይፋቸውን ቀጥቅጠው ማረሻ
ጦራቸውንም ማጭድ ያደርጋሉ::
ሕዝብ በሕዝብ ላይ ሰይፍ አያነሣም፤
ጦርነትንም ከእንግዲህ አይማሩም::
[5]እናንተ የያዕቆብ ቤት ሆይ፤ ኑ፤
በ*እግዚአብሔር* ብርሃን እንመላለስ::

**የእግዚአብሔር ቀን**

[6]የያዕቆብ ቤት የሆነውን፣
ሕዝብህን ትተሃል፤
እነርሱ በምሥራቅ ሰዎች ከንቱ አምልኮ
ተሞልተዋልና፤
እንደ ፍልስጥኤማውያን ያሟርታሉ፤
ከባዕዳን ጋር አገና ይማታሉ::
[7]ምድራቸው በብርና በወርቅ ተሞልታለች፤
ሀብታቸውም ልክ የለውም::
ምድራቸው በፈረሶች ተሞልታለች፤
የሠረገሎቻቸውም ብዛት ልክ የለውም::
[8]ምድራቸው በጣዖታት ተሞልታለች፤
ጣቶቻቸው ላበጁቸው፣
ለእጆቻቸው ሥራ ይሰግዳሉ::
[9]ሰው ዝቅ ብሎአል፤
የሰው ልጅም ተዋርዶአል፤
ስለዚህ በደላቸውን ይቅር አትበል[a]::
[10]*ከእግዚአብሔር* አስፈሪነት
ከግርማው ሽሽ፤
ወደ ዐለቶች ሂድ፤
በመሬትም ውስጥ ተሸሸግ::
[11]የእብሪተኛ ሰው ዐይን ይሰበራል፤
የሰዎችም ትዕቢት ይዋረዳል፤
በዚያን ቀን *እግዚአብሔር* ብቻውን ከፍ
ከፍ ይላል::
[12]የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር*
እብሪተኛውንና ትዕቢተኛውን ሁሉ፣
የተከራራውን በሙሉ
የሚያዋርድበት ቀን አለው::

1፥30 መዝ1፥3
1፥31 ኢሳ4፥4፤5፥24፤ 9፥18-19፤10፥17፤ 24፥6፤26፥11፤30፥27: 33፤33፥14፤34፥10፤ 66፥15-16:24፤ ኤር5፥14፤7፥20፤ 21፥12፤አብ1፥18፤ ሚል3፥2፤4፥1፤ ማቴ25፥41
2፥1 ኢሳ1፥1
2፥2 መዝ102፥15፤ ኢሳ11፥9፤24፥23፤ 25፥6:10፤27፥13፤ 56፥7፤57፥13፤65፥9: 25፤66፥20፤ኤር16፥19፤ 31፥23፤ዳን11፥45፤ ኢል3፥17፤ሚክ4፥7፤ ዘካ14፥10፤ሐሥ2፥17፤ ዕብ1፥2
2፥3 ዘዳ33፥19፤ መዝ137፥5፤ኢሳ1፥10፤ 33፥22፤45፥14:23፤ 49፥1:12:23፤51፥4:7፤ 55፥5፤60፥3-6:14፤ 66፥18፤ኤር3፥17፤ ኢል3፥2፤ሶፎ3፥8፤ ዘካ14፥2፤ሉቃ24፥47፤ ዮሐ4፥22
2፥4 ዘፍ49፥10፤ መዝ7፥6፤9፥19፤ 46፥9፤96፥13፤98፥9፤ ኢሳ1፥27፤3፥13፤ 9፥5:7፤11፥6-9፤ 32፥18፤42፥4፤51፥4፤ 57፥19፤65፥25፤ ኤር30፥10፤ዳን11፥45፤ ሆሴ2፥18፤ኢል3፥10: 14፤ሚክ4፥3፤ዘካ9፥10
2፥5 ኢሳ58፥1፤ 60፥1:19-20፤ ዮሐ1፥5:7
2፥6 ዘዳ18፥10፤ 31፥17፤2ነገ1፥2፤ 16፥7፤2ዜና26፥6፤ ምሳ6፥1፤ኢሳ44፥25፤ ኤር12፥7፤ሚክ5፥12
2፥7 ዘፍ41፥43፤ ዘዳ17፥16:17፤ መዝ17፥14፤ ኢሳ31፥1፤ሚክ5፥10

2፥8 2ዜና32፥19፤መዝ135፥15፤ኢሳ10፥9-11፤17፥8፤44፥17፤ ሚክ5፥13፤ ራእ9፥20 2፥9 ቍ 11:17፤ነሀ4፥5፤ መዝ62፥9፤ ኢሳ5፥15፤13፥11 2፥10 ቍ 19፤ዘኍ3፥11፤መዝ145፥12፤ ናሆ3፥11፤2ተሰ1፥9፤ራእ6፥15-16 2፥11 ቍ9:17:20፤ ነህ9፥29፤ ኢዮ40፥11፤መዝ46፥10፤ኢሳ3፥7:18፤4፥1:2፤5፥15:30፤7፥18፤10፥12፤ 17፥4:7፤24፥21፤25፥9፤26፥1፤ 27፥1፤37፥23፤ሕዝ31፥10፤ዕን2፥5
2፥12 2ሳሙ22፥28፤ኢዮ40፥11፤ መዝ59፥12፤76፥12፤ኢሳ13፥6:9፤ 22፥5:8: 12፤24፥4:21፤34፥8፤60፥11፤61፥2፤ኤር30፥7፤ሰቆ1፥12፤ ሕዝ7፥7፤30፥3፤ኢል1፥15፤2፥11፤ አሞ5፥18፤ሶፎ1፥14፤ሚል4፥1

[a]9 ወይም፣ *ከፍ አታድርጋቸው* ማለት ነው::

1፥31 *እሳቱንም፣* ቅጣትን የሚያመለክት ነው (33፥11-14፤ 34፥9-10 ይመ)::

*2፥1፤* ሁለተኛው መግቢያ ነው፣ ምናልባትም ከምዕራፍ 2-4 ወይም ከምዕራፍ 2-12 ጋር ሊዛመድ ይችላል (13፥1 ይመ)::

*2፥2-5፤* የ4፥2-6 ማብ ይመ::

*2፥2-4፤* ይህ ክፍል ከሚክ 4፥1-3 ጋር አንድ ነው:: "የእግዚአብሔር ተራራ" (የጽዮን ተራራ) የሚለው መሪ ሐሳብ በኢሳይያስ መጽሐፍ ተደጋግሞ ተጠቅሶአል፤ ይህም በመጨረሻው ዘመን ወደ ኢየሩሳሌም (ጽዮን) የሚመጡትን አይሁድና አሕዛብ በሚመለከቱ ልዩ ልዩ ክፍሎች ውስጥ በትንቢት መልክ ሰፍሮ ይገኛል (11፥9፤ 27፥13፤ 56፥7፤ 57፥13፤ 65፥25፤ 66፥20፤ 60፥3-5፤ ዘካ14፥16 ይመ):: አንዳንዶች በተጠቀሱት ምንባቦች የተገለጸው ሰላም ክርስቶስ ከመጣበት፣ ወንጌል ከተሰበከበት ጊዜ ይጀምርና በዳግም ምጽአቱ ይፈጸማል ሲሉ፣ ሌሎች ደግሞ ክርስቶስ ዳግም መጥቶ በምድር ላይ በሚነግሥበት ጊዜ፣ ስለሚፈጸመው ሁኔታ የተነገረ ትንቢት ነው ይላሉ::

2፥2 *በዘመኑም ፍጻሜ፤* በአጠቃላይ የወደፊቱን ሁናቴ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ዘፍ 49፥1 ይመ)፤ ነገር ግን የመሲሑን ዘመን በግልጽ የሚያሳይ ይመስላል:: እንደ እውነቱ ከሆነ የዘመኑ ፍጻሜ የሚጀምረው ክርስቶስ በሥጋ በተገለጠበት ጊዜ ሲሆን (ሐሥ 2፥17፤ ዕብ 1፥2)፣ የሚደመደመው በዳግም ምጽአቱ ነው::

2፥4 *ሰይፋቸውን ቀጥቅጠው ማረሻ ... ያደርጋሉ፤* ይህ በኢል 3፥10 ላይ በሌላ መልኩ ተገልብጦ ተገልጾአል:: እዚህ ላይ የተጠቀሰው ማረሻ ከዕርፍ ጋር የተያያዘ ሆኖ መሬቱን እየተረተረ የሚሄድ ሹል ብረት ነው:: በጥንት ጊዜ የነበሩ ማረሻዎች እንዳሁኑ ዘመን ብረት አልነበሩም::

2፥6 *በምሥራቅ፤* ሶርያንና መስጴጦምያን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል:: *እንደ ፍልስጥኤማውያን ያሟርታሉ፤* እነዚህን ስለ መሳሰሉ ልምምዶች 1ሳሙ 6፥2፤ ዘዳ 18፥10-11 ይመ::

2፥7 *በብርና በወርቅ ... በፈረሶች፤* አንድ ንጉሥ እንዲህ ያሉትን ነገሮች በብዛት ማካበት እንደ ሌለበት ተጽፎ (ዘዳ 17፥16-17):: ብዙውን ጊዜ እነዚህ ነገሮች ሰው በእግዚአብሔር እንዳይታመን የልብ ልብ ይሰጡታልና (31፥1 ይመ)::

*2:10:19:21፤* እነዚህ ጥቅሶች በቍ 21 ላይ ከተጠቀሰው ከፍተኛ ችግር ሰው ራሱን የሚደብቅበት ሊያገኝ እንደማይችል ያመለክታሉ:: አብዛኞዎቹ ስንኞቻቸውም ይመሳሰላሉ::

2፥10 *ከግርማው፤* ይህ ቃል በዕብራይስጥ ስለ ሰው ከተነገረ፣ "ትዕቢት" የሚል ትርጒም ይሰጣል:: ትዕቢት ደግሞ ሰው ራሱን እንደ አምላክ አድርጎ እንዲያይ የሚገፋፋው ኀይል ነው (14፥13-14 ይመ):: *ዐለቶች ... በመሬትም፣* እስራኤላውያን ጭንቅና መከራ በሚመጣባቸው ጊዜ፣ በመሬት ውስጥ ባሉ ዋሻዎችና ጕድጓዶች ውስጥ እንደሚሸሸጉ ያመለክታል (መሳ 6፥1-2፤ 1ሳሙ 13፥6 ይመ)::

2፥11:17:20 *በዚያን ቀን፤* ይህ ሐረግ ከምዕራፍ 2-4 ባለው ክፍል ሰባት ጊዜ ተጽፎአል (3፥7:18፤ 4፥1-2 ይመ):: የጌታ ቀን (ቍ 12 ይመ) እግዚአብሔር በሕዝቦች ጕዳይ የማያወላውልና ቈራጥ ውሳኔ ለመስጠት ጣልቃ የሚገባበት የፍርድ ወይም የበረከት ቀን (ሶፎ 1፥14-2፥3 ይመ) ነው:: አሦርና ባቢሎን በኢሳይያስ ዘመን የእግዚአብሔርን ፍርድ በይሁዳ ላይ እንዲፈጽሙ የታዘዙ ናቸው (5፥30)::

[13]ረዥምና ከፍ ከፍ ያሉትን የሊባኖስ ዝግባዎች ሁሉ፣
የባሳንን የወርካ ዛፎች ሁሉ፣
[14]ታላላቁን ተራራ ሁሉ፣
ከፍ ያለው ኰረብታ ሁሉ፣
[15]ረጃጅሙን ግንብ ሁሉ፣
የተመሸገውን ቅጥር ሁሉ፣
[16]የተርሴስን መርከቦች[*] ሁሉ፣
የክብር ጀልባዎችን ሁሉ የሚያዋርድበት ቀን አለው::
[17]የሰው እብሪት ይዋረዳል፤
የሰውም ኵራት ይወድቃል፤
በዚያን ቀን እግዚአብሔር ብቻ ከፍ ከፍ ይላል፤
[18] ጣዖቶች ሁሉ ፈጽሞ ይወድማሉ::

[19]እግዚአብሔር ምድርን ለማናወጥ በሚነሣበት ጊዜ፣
ሰዎች ከአስፈሪነቱ
ከግርማውም የተነሣ፣
ወደ ዐለት ዋሻ
ወደ መሬትም ጉድጓድ ለመሸሸግ ይሮጣሉ።
[20]በዚያን ቀን ሰዎች
ሊያመልኳቸው ያበጇቸውን፣
የብርና የወርቅ ጣዖቶቻቸውን
ለፍልፈልና ለሌሊት ወፍ ይወረውራሉ::
[21]እግዚአብሔር ምድርን ለማናወጥ በሚነሣበት ጊዜ፣
ሰዎች ከአስፈሪነቱ
እንዲሁም ከግርማው የተነሣ፣
ወደ ድንጋይ ዋሻ፣
ወደ ዐለት ስንጣቂ ሮጠው ይገባሉ::
[22]እስትንፋስ አፍንጫው ላይ ባለች
በሰው አትታመኑ፤
ከቶ ምን የሚበጅ ነገር አለው!

## በኢየሩሳሌምና በይሁዳ ላይ የሚመጣ ፍርድ

**3** እነሆ፤ ጌታ፣
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ከኢየሩሳሌምና ከይሁዳ
ድጋፉንና ርዳታውን፣
የምግብና የውሃ ርዳታውን ሁሉ ይነሣል፤
[2]ጀግናውንና ተዋጊውን፣
ፈራጁንና ነቢዩን፣
አስማተኛውንና ሽማግሌውን፣
[3]የአምሳ አለቃውንና ባለ ማዕረጉን፣
አማካሪውንና ጠቢቡን የእጅ ባለሙያ፣
ብልኁንም ምትሀተኛ ይነሣል::

[4]ልጆችን መሪዎቻቸው አደርጋለሁ፤
ያልበሰሉ ሕፃናትም ይገዟቸዋል::
[5]ሕዝብ እርስ በርሱ ይጨቋቈናል፤
ሰው በሰው ላይ፤ ባልንጀራ በባልንጀራው ላይ፣
ወጣቱ በሽማግሌው ላይ፣
ተራው ሰው በተከበረው ላይ ይነሣል::

[6]ሰውም በአባቱ ቤት
ከወንድሞቹ አንዱን ይዞ፣
"አንተ ልብስ ስላለህ መሪ ሁነን፤
ይህንንም የፍርስራሽ ክምር ግዛ" ይለዋል::
[7]እርሱ ግን በዚያ ቀን ድምፁን ከፍ አድርጎ፣
"እኔ መፍትሔ አልሆንም፤
በቤቴም ልብስና ምግብ የለኝም፤
የሕዝብ መሪ አታድርጉኝ" ይላል::

[8]ኢየሩሳሌም ትንገዳገዳለች፤
ይሁዳም ለመውደቅ ተቃርባለች፤
ንግግራቸውም ሆነ ድርጊታቸው እግዚአብሔርን የሚቃወም፣
የክብሩንም መገኘት የሚያቃልል ነውና::
[9]የፊታቸው ገጽታ ይመሰክርባቸዋል፤
ኀጢአታቸውን እንደ ሰዶም በይፋ ይናገራሉ፤
አይደብቁትምም፤
ጥፋትን በራሳቸው ላይ ስላመጡ::
ወዮላቸው!

[10]ጻድቃን መልካም ነገር እንደሚያገኙ ንገሯቸው፤
የሥራቸውን ፍሬ ያበላሉና::

2፥13 መሳ9፥15፤ መዝ22፥12፤ ኢሳ10፥33:34፤ 29፥17፤ሕዝ27፥5፤ ዘካ11፥2
2፥14 ኢሳ30፥25፤ 40፥4
2፥15 ኢሳ25፥2:12፤ 30፥25፤32፥14፤33፥18፤ ሶፎ1፥16
2፥16 ዘፍ10፥4፤ 1ነገ9፥26
2፥17 ቍ9:11፤ 2ሳሙ22፥28፤ ኢዮ40፥11
2፥18 ዘጸ9፥21፤ 1ሳሙ5፥2፤ኢሳ21፥9፤ ኤር10፥11፤ ሕዝ36፥25፤ሚክ5፥13
2፥19 ቍ21፤ ዘጸ2፥25፤መሳ6፥2፤ ኢዮ9፥6፤30፥6፤ መዝ145፥12፤ ኢሳ7፥19፤14፥16፤ ሉቃ23፥30፤ ዕብ12፥26፤ራእ6፥15
2፥20 ቍ11፤ ዘሌ11፥19፤ ኢዮ22፥24፤ ሕዝ7፥19-20፤14፥6፤ 36፥25፤ራእ9፥20
2፥21 ቍ19፤ ዘፀ33፥22፤መዝ145፥12፤ ኢሳ33፥10
2፥22 ዘፍ2፥7፤ ኢዮ12፥19፤መዝ8፥4፤ 18፥42፤118፥6:8፤ 144፥3:4፤146፥3፤ ኢሳ17፥13፤29፥5፤ 40፥15፤51፥12፤ ኤር17፥5፤ያዕ4፥14
3፥1 ዘሌ26፥26፤ መዝ18፥18፤ ኢሳ5፥13፤65፥13፤ ሕዝ4፥16፤አሞ4፥6
3፥2 ዘጸ18፥10፤ ኢሳ9፥14-15፤ሕዝ17፥13
3፥3 2ነገ1፥9፤ 24፥14፤ ኢዮ22፥8፤ መክ10፥11፤ ኤር8፥17
3፥4 ቍ12፤ መክ10፥16
3፥5 መዝ28፥3፤ ኢሳ9፥19፤ኤር9፥8፤ ሚክ7፥2:6
3፥7 ኢሳ2፥11፤24፥2፤ ኤር30፥12፤ሕዝ34፥4፤ሆሴ5፥13፤ኢል1፥16 3፥8 2ዜና33፥6፤ ኢዮ1፥11፤ መዝ73፥9:11፤ ኢሳ1፥7፤9፥15:17፤28፥15፤30፥9፤ 59፥3:13፤65፥7 3፥9 ዘፍ13፥13፤ዘኍ32፥23፤2ዜና34፥24፤ምሳ8፥36፤ ኢሳ59፥12፤ ኤር14፥7፤ ሆሴ5፥5፤ሮሜ6፥23 3፥10 ዘፍ15፥1፤ ዘዳ5፥33፤12፥28፤28፥1-14፤መዝ37፥17፤128፥2፤ኤር22፥15

[*]16 ወይም *የንግድ መርከቦች* ማለት ነው

2፥13 *የሊባኖስ ዝግባዎች፤* እግዚአብሔር ብቻ ከፍ ይል ዘንድ ግዑዛን ፍጥረታት እንኳ በፊቱ ዝቅ ዝቅ ይላሉ (ቍ 11)። *ባሳን፤* ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተ ምሥራቅ፣ ከገለዓድ በስተ ሰሜን ያለ አገር ነው:: በወርካ ዛፍና (ሕዝ 27፥6) በእንስሳት (ሕዝ 39፥18) በጣም የታወቀ ነው::

2፥16 *የተርሴስን መርከቦች፤* እነዚህ መርከቦች ሰሎሞንና (1ነገ 10፥22) ፊንቃውያን (ኢሳ 23፥1:14) ባሕሩን ለማቋረጥና በሩቅ ቦታ የሚካሄደውን ንግድ ሁሉ ለመቈጣጠር እንደ ተጠቀሙባቸው ያሉ ናቸው::

*2፥20፤* የአምልኮ ጣዖት ከንቱነት በኢሳይያስ መጽሐፍ ተደጋግሞ ተጠቅሷል (ለምሳሌ 30፥22፤ 31፥7፤ 40፥19-20፤ 44:9-20 ይመ)፤ እንዲሁም የ40፥18-20 ማብ ይመ::

2፥22 *በሰው አትታመኑ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ሰውን ተው" ወይም፣ "ሰውን ተስፋ አታድርጉ" ማለት ነው:: ቃሉ 53፥3 ላይ የተጠቀሰውን የመሲሑን በሰዎች ዘንድ መናቅና መጠላት ይገልጣል:: መሲሑ ሊታመኑበትና ሊከበር ሲገባ፣ በሰዎች ዘንድ መናቁ መዋረዱ በምፀት ተገልጦአል ከፍ ከፍ ማለት የሚገባው እርሱ ብቻ ሆኖ ሳለ ደካማ ለሆኑ መሪዎች በስሕተት ዕልፍ እንዲሰጥ ተደረገ::

*3፥1-3፤* መሪዎች በሞት ይወገዳሉ፤ ወይም ደግሞ በግዞት ወደ ሌላ ቦታ/አገር/ ይወሰዳሉ (2ነገ 24፥14፤ 25፥18-21 ይመ)::

3፥2-3 *አስማተኛውንና ... ምትሀተኛ፤* አድራጎታቸው የተወገዘ መተተኞችና በአብዛ አሰማት የሚሠሩ (ዘዳ 18፥10፤ ኤር 8፥17)፤ ሕጋዊ የሆነውና ያልሆነው ድጋፍ ሁሉ በምርኮ ይወሰዳል፣ ወይም ይጋዛል (2ነገ 24፥14-16፤ ሆሴ 3፥4 ይመ)::

3፥3 *የአምሳ አለቃው፤* ወታደሮችን በአምሳ በአምሳ እየከፈሉ መመደብ የተለመደ አሠራር ነበር (2ነገ 1፥9 ይመ)፤ እንዲህ ዐይነቱ ምደባ በወታደሩ ዘንድ ብቻ ሳይሆን (ዘፀ 18፥25)፣ በሌላውም ክፍል የተለመደ ነበር::

3፥6 አንድን ሰው መሪ እንዲሆን ማስገደድ የተለመደ አይደለም፤ አስፈላጊም አልነበረም:: በዚያን ጊዜ በኅብረተሰቡ ዘንድ ታይቶና ተሰምቶ በማይታወቅ ሁኔታ ሰባት ሴቶች አንዱን ወንድ እንደሚይዙት በ4፥1 ላይ ተጽፎአል:: *ልብስ ስላለህ፤* ምናልባት ያ ሰው (ወንድም) እንደ ሌሎቹ አልደኸየ ይሆናል:: *የፍርስራሽ ክምር፤* ኢየሩሳሌምን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ቍ 8)::

3፥7:18 *በዚያ ቀን፤* የ2፥11:17:20 ማብ ይመ::

3፥8 *ይሁዳም ለመውደቅ ተቃርባለች፤* ከአንድ መቶ አምሳ ዓመት በኋላ፣ ተጠቃሎአል::

3፥9 *ሰዶም፤* የ1፥9-10 ማብ ይመ::

[11]በደለኞች ወዮላቸው፤ ጥፋት ይመጣባቸዋል፤
 የእጃቸውን ያገኛሉና።

[12]ወጣቶች ሕዝቤን ያስጨንቃሉ፤
 ሴቶችም ይገዟቸዋል።
ሕዝቤ ሆይ፤ መሪዎችህ አሳስተውሃል፤
 ከመንገድህም መልሰውሃል።

[13]እግዚአብሔር በፍርድ ወንበር ላይ ተቀምጦአል፤
 በሕዝቡም ላይ ለመፍረድ ተነሥቶአል።
[14]እግዚአብሔር፣
 ከአለቆችና ከሕዝቡ ሽማግሌዎች ጋር እንዲህ
  ሲል ይፋረዳል፤
"የወይኔን ቦታ ያጠፋችሁ እናንተ ናችሁ፤
 ከድኾች የዘረፋችሁትም በቤታችሁ ይገኛል፤
[15]ሕዝቤን በችግር ስታደቁት፣
 የድኾችንም ፊት በሐዘን ስታገረጡት ምን
  ማለታችሁ ነው?"
   ይላል ጌታ፣
   የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር።

[16]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
 የጽዮን ሴቶች ኰርተዋል፤
ዐንገታቸውን እያሰገጉ፣
 በዐይናቸውም እየጠቀሱ ይሄዳሉ፤
እየተቈነኑ በመራመድ፣
 የእግራቸውን ዐልቦ ያቃጭላሉ።
[17]ስለዚህ፣ ጌታ በጽዮን ሴቶች ዐናት ላይ
  ቈረቈር ያመጣል፤
 እግዚአብሔርም ራሳቸውን በሀ ያደርጋል።

[18]በዚያም ቀን ጌታ የክብር ጌጣቸውን ይነ ጥቃቸዋል፤ የእግር አንባሩን፣ የጠጕር ጌጡን፣ የጨረቃ ቅርጽ ያለውን የዐንገት ጌጥ፣ [19]የጆሮ ጉትቻውን፣ የእጅ አንባሩን፣ የፊት መሸ ፈኛውን፣ [20]የራስ መሸፈኛውን፣ ዐልቦውን፣ ሻሹን፣ የሽቶ ብልቃጡን፣ አሸንክታቡን፣ [21]የጣት ቀለበቶችንና የአፍንጫ ቀለበቶችን፣ [22]ያማረውን ቀሚስ፣ የውስጥ ልብሱን፣ ካባውን፣ የእጅ ቦርሳውን፣ [23]መስታወቱን፣ ከጥሩ በፍታ የተሠራውን ልብስ፣ የራስ ጌጡን፣ ዐይነ ርግቡን ሁሉ ይነጥቃቸዋል።

[24]በሽቶ ፈንታ ግማት፣
 በሻሽ ፈንታ ገመድ፣
አምሮ በተሠራ ጠጕር ፈንታ ቡሀነት፣
 ባማረ ልብስ ፈንታ ማቅ፣
 በውበትም ፈንታ ጠባሳ ይሆናል።
[25]ወንዶቻችሁ በሰይፍ ስለት፣
 ተዋጊዎቻችሁ በጦርነት ይወድቃሉ።
[26]የጽዮን ደጆች ያዝናሉ፣ ያለቅሳሉም፤
 እርሷም ተራቍታ በመሬት ላይ ትቀመጣለች።

4 በዚያን ቀን ሰባት ሴቶች
 አንዱን ወንድ ይዘው፣
"የራሳችንን ምግብ እንበላለን፤
 የራሳችንንም ልብስ እንለብሳለን፤
በአንተ ስም ብቻ እንጠራ፣
 ውርደታችንን አስቀርልን" ይሉታል።

## የእግዚአብሔር ዛፍ ቅርንጫፍ

[2]በዚያን ቀን የእግዚአብሔር ዛፍ ቅርንጫፍ ያማረና የከበረ ይሆናል፤ የምድሪቱም ፍሬ ከጥፋት ለተረፈው የእስራኤል ወገን ኵራትና ክብር ይሆናል። [3]በጽዮን የቀሩት፣ በኢየሩ ሳሌምም የተረፉት፣ በኢየሩሳሌም በሕ ይወት ከተመዘገቡት ሁሉ ጋር ቅዱሳን ተብ ለው ይጠራሉ። [4]ጌታ የጽዮንን ሴቶች እድፍ ያጥባል፤ ኢየሩሳሌምንም ከተነከረችበት ደም

3፥11 ዘዳ28፥15-68፤ 2ዜና6፥23፤ኢዮ9፥13፤ ኢሳ57፥20፤ሉ፫21፥14፤ ሰቆ5፥16፤ሕዝ24፥14
3፥12 ቍ4፤ ኢሳ9፥16፤19፥14፤ 28፥7፤29፥9፤ ኤር23፥13፤25፥16፤ ሚክ3፥5
3፥13 ኢዮ10፥2፤ መዝ82፥1፤ኢሳ2፥4
3፥14 1ሳሙ12፥7፤ ኢዮ22፥4፤24፥9፤ ኢሳ11፥4፤25፥4፤ ያዕ2፥6
3፥15 ኢዮ24፥14፤ መዝ94፥5፤ኢሳ5፥7፤ 10፥6፤11፥4፤26፥6፤ 29፥19፤32፥6፤51፥23
3፥16 ኢዮ15፥25፤ መሐ3፥11
3፥17 ቍ24፤ ሕዝ27፥31፤አሞ8፥10
3፥18 ዘፍ41፥42፤ መሳ8፥21፤ኢሳ2፥11
3፥19 ዘፍ24፥47፤ ሕዝ16፥11-12
3፥20 ዘፀ39፥28፤ ሕዝ24፥17፡23፤ 44፥18
3፥21 ዘፍ24፥22
3፥22 ሩት3፥15
3፥23 ዘፀ29፥6፤ መሐ3፥11፤ ኢሳ61፥3፤62፥3፤ ሕዝ16፥10፤23፥26
3፥24 ቍ17፤ ዘፍ37፥34፤ዘሌ13፥40፤ 2ሳሙ10፥4፤አስ2፥12፤ ኢዮ1፥20፤16፥15፤ ምሳ31፥24፤ ኢሳ4፥4፤20፥2፡4፤ ኤር4፥8፤ ሰቆ2፥10፤ ሕዝ27፥30-31፤ የና3፥5-8፤1ጴጥ3፥3
3፥25 ኢሳ1፥20፤ ኤር15፥8
3፥26 ዘሌ26፥31፤ ኢዮ2፥13፤መዝ137፥1፤ ኢሳ14፥31፤24፥4፡7፡12፤29፥2፤33፥9፤45፥2፤ኤር4፥28፤14፥2፤ሰቆ4፥5
4፥1 ዘፍ30፥23፤ኢሳ2፥11፤ 13፥12፤32፥9፤2ተሰ3፥12
4፥2 መዝ72፥16፤ኢሳ1፥9፤2፥11፤ 11፥1-5፤33፥17፤52፥13፤ 53፥2፤60፥15፤ኤር23፥5-6፤33፥15-16፤ሕዝ17፥22፤34፥29፤36፥8፤ ዘካ3፥8፤6፥12፤4፥3 ዘፀ19፥6፤መዝ56፥8፤87፥6፤ኢሳ1፥9፡26፤26፥2፤ 45፥25፤52፥1፤60፥21፤ኢሊ3፥17፤አብ1፥17፤ሰፎ3፥13፤ሉቃ10፥20፤ ሮሜ11፥5 4፥4 መዝ51፥2፤ ሚል3፥11፤ኢሳ1፥15፡31፤3፥24፤ 28፥6፤30፥30፤ዘካ13፥9፤ማቴ3፥11፤ ሉቃ3፥17

*3፥12፤* በመካከለኛው ምሥራቅ በወጣት ወንዶችም ሆነ ሴቶች መገዛት አይታሰብም ነበር።

3፥14 *የወይኔን ቦታ፤* እስራኤልን ይወክላል (5፥1 ይመ)።

*3፥15፤* ሰዎች እህል በድንጋይ ወፍጮ እንደሚፈጩ፣ መሪዎችም ድኾውን ይፈጩ ነበር።

*3፥16-24፤* ጌጣ ጌጥ ማብዛት እንደማይገባ የሚገልጸውን የአዲስ ኪዳን ማስጠንቀቂያ በ1ጴጥ 3፥3-4 ይመ።

3፥16 *ይሄዳሉ፤ እየተቈነኑ በመራመድ፤* በመካከለኛው ምሥራቅ የአንድ ሰው አረማመድ ልዩ ጠባዩን ይገልጣል ተብሎ ይታመናል። የእግር ዐልቦ ድምፅ እንዳያሰማ ዝግ ብሎ መራመድ አስፈላጊ መሆኑ አያጠያይቅም።

3፥17 *በሀ፤* መመለጥ በአደጋ ጊዜ ከሚያጋጥም ሐዘን የተነሣ ሊመጣ ይችላል (ቍ 24፡15፥2 ይመ)።

3፥18 *የጨረቃ ቅርጽ ያለውን የዐንገት ጌጥ፤* ምናልባትም የጨረቃን ቅርጽ የያዘ ሊሆን ይችላል። የታወቀውን የጨረቃን አምላክ ማክበርን ያመለክታል።

3፥20 *የራስ መሸፈኛውን፤* ምናልባት የጥምጥም ዐይነት ሊሆን ይችላል (ሕዝ 24፥17፡23 ይመ)።

3፥21 *የጣት ቀለበቶችንና፤* ማኅተም ያለባቸው የሥልጣን ማረጋገጫ ምልክት ናቸው (ዘፍ 41፥42 እና ማብ ይመ)። *የአፍንጫ ቀለበቶችን፤* የአፍንጫ ቀለበት አንዳንድ ጊዜ የሚሠራው ከወርቅ ሲሆን፣ ሙሽራ ታጌጥበታለች።

3፥24 *ገመድ ...፤ ጠባሳ፤* ምርኮኞች እንደ ከብት ስለሚቈጠሩ በገመድ ታስረው ይወሰዱ፤ አንዳንዶም በጋለ ብረት ይጠበሱ ነበር።

3፥26 *የጽዮን ደጆች፤* በመዝሙር 24፥7፡9 እንደ ተገለጸው፣ በሮቹ በሰውኛ ዘይቤ ተገልጸዋል። በዚያ ይሰበሰብ የነበረው ሕዝብ ተማርኮ ስለ ሄደ ያለቅሳሉ።

4፥1-2 *በዚያን ቀን፤* የ2፥2 ማብ እና 2፥11፡17፡20 ይመ። ከፍርድ በኋላ ድነት ይመጣል።

*4፥1፤* የ3፥6 ማብ ይመ። ጦርነት ወንዶችን በመጨረስ (3፥25፤ 3፥12 ይመ) ሴቶችን ያለ ልጅና፣ ያለ ባል ያስቀራቸዋል (54፥4 ይመ)።

*4፥2-6፤* በምዕራፍ 5 ከተገለጸው ረጅም የክስና የፍርድ መልእክት በፊት የተሰጠ የመዋጀት ንግር ነው። ይህም በምዕራፍ 1 ላይ የተጠቀሰውን ረጅም የክስና የፍርድ መልእክት ተከትሎ የቀረበውን፣ በ2፥2-5 የሚገኘውን ሐሳብ ሚዛናዊ ያደርገዋል (በ1፥1-31 ያለውን ማብ ይመ)። እነዚህ ሁለት የመዋጀት ንግር ቃላት እርስ በርሳቸው ይደጋገፋሉ።

4፥2-3 *ለተረፈው ... ወገን ... የቀሩት፤* የ1፥9 ማብ ይመ።

4፥2 *ቅርንጫፍ፤* የመሲሑን ስም የሚያመለክት ሲሆን፣ "ቍጥቋጥ" (11፥1) እና "ቡቃያ" (53፥2) ከተባለው የዳዊት ዘር ከሆነው ጋር ይገናዘባል፤ ይሁን እንጂ አንዳንዶች፣ "ቅርንጫፍ" የሚለው ይሁዳን ነው ይላሉ። *ኵራትና፤* የመሲሑን የአገዛዝ ጊዜ ከሚያመለክተው ከምድሪቱ ፍሬያማ መሆን የተነሣ የሚመጣ ተገቢ የሆነ ኵራት ነው (መዝ 72፥3፡6፡16 ይመ)። በ2፥11፡17 ላይ ካለው ጋር ያነጻጽሩ። *ክብር፤* እዚህም ላይ የምድሪቱ ፍሬያማነት የእስራኤል ክብር እንደ ሆነ ተገልጾአል፤ በ46፥13 ላይ የእግዚአብሔር ማዳን ለምድሪቱ ክብሯ እንደ ሆነ ተጠቅሶአል፤ በ60፥19 ላይ ደግሞ ክብሯ እግዚአብሔር ራሱ ነው።

4፥3 *ቅዱሳን፤* ለእግዚአብሔር የተለዩ ማለት ነው፤ 1፥26፤ 6፥13፤ ዘካ 14፥20 ይመ።

4፥4 *በፍርድና በሚያቃጥል፤* የሚያጠራ እሳት በ1፥25፤ 48፥10 ላይ ተገልጾአል።

በፍርድና በሚያቃጥል መንፈስ[a] ያነጻታል። [5]ከዚያም እግዚአብሔር በጽዮን ተራራ ላይና በዚያ በሚሰበሰቡትም ሁሉ ላይ በቀን ደመናን ጢስን፣ በሌሊትም የሚንበለበለውን የእሳት ብርሃን ይፈጥራል፤ በክብሩ ሁሉ ላይ መጋረጃ ይሆናል፤ [6]ከቀኑ ሙቀት ጥላና መከለያ፣ ከውሽንፍርና ከዝናብም መጠጊያና መሸሸጊያ ስፍራ ይሆናል።

## ስለ ወይን ቦታ የተነገረ ቅኔ

**5** ስለ ወዳጄ፣
ደግሞም ስለ ወይን ቦታው ልዘምር፤
ወዳጄ በለምለም ኰረብታ ላይ
የወይን ቦታ ነበረው።
[2]መሬቱን ቈፈረ፤ ድንጋይንም ለቅሞ አወጣ፤
ምርጥ የሆነውንም ወይን ተከለበት።
በመካከሉ መጠበቂያ ማማ ሠራ፤
የወይን መጭመቂያ ጕድጓድም አበጀ፤
ከዚያ መልካም ፍሬ ያፈራል ብሎ አሰበ፤
ነገር ግን ኮምጣጣ ፍሬ አፈራ።
[3]"እናንት በኢየሩሳሌም የምትኖሩና የይሁዳ ሰዎች ሆይ፤
በእኔና በወይኔ ቦታ መካከል እስቲ ፍረዱ።
[4]ከዚህ ካደረግሁለት በላይ ለወይኔ ቦታ ምን ሊደረግለት ይገባ ነበር?
መልካም የወይን ፍሬ ያፈራል ብዬ ስጠብቅ
ለምን ኮምጣጣ ፍሬ አፈራ?
[5]እንግዲህ በወይኔ ቦታ
ምን እንደማደርግ ልንገራችሁ፤
ዐጥሩን እነቅላለሁ፤
ለጥፋት ይጋለጣል፤
ግንቡንም አፈርሳለሁ፣
መረጋገጫም ይሆናል።
[6]የማይኰተኰትና የማይታረም
ጠፍ መሬት አደርገዋለሁ፤
ኵርንችትና እሾኽም ይበቅልበታል፤
ዝናብም እንዳይዘንብበት
ደመናዎችን አዝዛለሁ።"
[7]የሰራዊት ጌታ የእግዚአብሔር
የወይን ቦታው የእስራኤል ቤት ነው፤
የይሁዳ ሰዎችም
የደስታው አትክልት ናቸው።
ፍትሕን ፈለገ፤ ነገር ግን ደም ማፍሰስን አየ፤
ጽድቅን ፈለገ፤ ነገር ግን የጭንቅን ጩኸት ሰማ።

## ወዮታና ፍርድ

[8]ስፍራ ለሌሎች እስከማይተርፍ፣
ቤትን በቤት ላይ በመጨመር፣
መሬትን ከመሬት ጋር በማያያዝ፣
ለብቻችሁ በምድር ተስፋፍታችሁ ለምትኖሩ
ወዮላችሁ!
[9]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ጆሮዬ እየሰማ
እንዲህ ሲል ተናገረ፤
"ታላላቅ ቤቶች ወና ይቀራሉ፣
የሚያማምሩም ቤቶች ኗሪ ያጣሉ።
[10]ከሩብ ጋሻ[b] የወይን ቦታ አንድ የባዶስ መስፈሪያ ያህል የወይን ጭማቂ ብቻ ይገኛል፤
አንድ የቆሮስ መስፈሪያ ዘር ተዘርቶ አንድ የኢፍ መስፈሪያ እህል ብቻ ይሰጣል።"[c]
[11]የሚያሰክር መጠጥ ፍለጋ
ማልደው ለሚነሡ፣
እስኪያነዳቸውም ወይን በመጠጣት
ሌሊቱን ለሚያነጉ ወዮላቸው!
[12]በግብዣቸው ላይ በገናና መሰንቆ፣
ከበሮና ዋሽንት እንዲሁም የወይን ጠጅ
አለ፤
ነገር ግን ለእግዚአብሔር ሥራ ቦታ አልሰጡም፤
ለእጆቹም ሥራ ክብር አላሳዩም።

4፥5 ዘፀ13፥21፤ መዝ18፥11፤ ኢሳ35፥2፤ 41፥20፤58፥8፤60፥1፤ 65፥18፤ራእ7፥15፤ 14፥1
4፥6 ዘሌ23፥34-43፤ መዝ27፥5፤55፥8፤ ኢሳ8፥14፤14፥32፤ 25፥4፤30፥2፤57፥13፤ ሕዝ11፥16
5፥1 መዝ80፥8-9፤ ኢሳ27፥2፤ዮሐ15፥1
5፥2 ዘፀ15፥17፤ 1ሳሙ2፥9፤ኢዮ24፥11፤ ኢሳ16፥8፤27፥3፤ 31፥5፤49፥8፤ ማቴ21፥19፡33፤ ማር11፥13፤ሉቃ13፥6
5፥3 ማቴ21፥40
5፥4 2ዜና36፥15፤ ኤር2፥5-7፡21፤24፥2፤ 29፥17፤ሚክ6፥3-4፤ ማቴ23፥37
5፥5 2ዜና36፥21፤ መዝ80፥12፤ ኢሳ6፥12፤10፥6፤ 22፥5፤26፥6፤27፥10፤ 28፥3፡18፤41፥25፤ 63፥3፤ኤር12፥10፤ 34፥22፤ሰቆ1፥15፤ ሆሴ2፥12፤ሚክ7፥10፤ ሚል4፥3፤ሉቃ21፥24
5፥6 ቍ10፡17፤ ዘፍ6፥13፤ዘሌ26፥32፤ ዘዳ28፥24፤2ሳሙ1፥21፤ 23፥6፤ኢሳ6፥13፤ 7፥23፡24፤32፥13፤ 34፥13፤49፥17፡19፤ 51፥3፤55፥13፤ ሕዝ28፥24፤ሆሴ2፥12፤ ኢል1፥10፤አሞ4፥7፤ ዕብ6፥8
5፥7 መዝ12፥5፤ 80፥8፤ኢሳ1፥21፤ 10፥2፤17፥10፤ 18፥5፤29፥21፤32፥7፤ 37፥30፤59፥15፤ 61፥8፤ሕዝ9፥9፤ 22፥29
5፥8 ቍ11፡18፡20፤ ኢዮ20፥19፤ኢሳ6፥5፤ 10፥1፤24፥16፤ ኤር22፥13፤ሚክ2፥2፤ ዕን2፥9-12
5፥9 ኢሳ6፥11-12፤ 22፥14፤ኤር44፥11፤ማቴ23፥38
5፥10 ቍ6፤ ዘሌ26፥26፤ዘዳ28፥38፤ዘካ8፥10 5፥11 ቍ8፤ 1ሳሙ25፥36፤ምሳ23፥29-30 5፥12 1ሳሙ12፥24፤ኢዮ21፥12፤ መዝ28፥5፤68፥25፤ኢሳ24፥8፤ሕዝ26፥13

[a]4 ወይም *በእግዚአብሔር መንፈስ* ማለት ነው።
[b]10 በዕብራይስጥ፣ *ሩብ ጋሻ* መሬት በዐሥር ጥማድ በሬ በአንድ ቀን የሚታረስ ነው።
[c]10 ምናልባት አንድ ባዶስ ሀያ ሁለት ሊትር ያህል ነው።
አንድ የቆሮስ መስፈሪያ ሰማኒያ ኪሎ ግራም ያህል ነው።
አንድ የኢፍ መስፈሪያ ዐሥራ ስምንት ኪሎ ግራም ያህል ነው።

4፥5-6 *ደመና ... የእሳት ... መጋረጃ፤* እነዚህ ቃላት እስራኤላውያን በምድረ በዳ ይጓዙ በነበሩበት ጊዜ፣ እግዚአብሔር በደመናና በእሳት ዐምድ ሲመራቸውና ሲጠብቃቸው የነበረበትን ሁኔታ ያስታውሳል (ዘፀ 13፥21-22፤ 14፥21-22 ይመ)። ኢሳይያስ እስራኤል ከግብፅ የወጡበትን ጊዜ በመደጋገም ይጠቅሳል (11፥15-16፤ 31፥5፤ 51፥10 ይመ)።

4፥5 *በክብሩ፤* የእግዚአብሔር በዚያ ስፍራ መገኘት በሚንበለበል የእሳት ብርሃን ተገልጦአል (ዘፀ 16፥10፤ 24፥17፤ 40፥34-35 ይመ)። *መጋረጃ፤* የጢሱን ደመና የሚያመለክት ነው።

*4፥6፤* በደመናና በእሳት የተገለጠው ህልዎተ እግዚአብሔር የተዋጀችውን ጽዮንን ይጠብቃል (ከመዝ 121፥5-6 ጋር ያነጻጽሩ)።

*5፥1-30፤* የ1፥1-31 ማብ ይመ።

5፥1 *ወዳጄ፤* እግዚአብሔርን የሚያመለክት ነው። *የወይን ቦታ፤* እስራኤልን ያመለክታል (ቍ 7፡3፥14፤ መዝ 80፥8-16 ይመ)። ኢየሱስ በጢሰኞነት ስለሚያርሱ ገበሬዎች የተናገረው ምሳሌ (ማቴ 21፥33-44፤ ማር 12፥1-11፤ ሉቃ 20፥9-18) በዚህ መዝሙር ላይ የተመሠረተ ሊሆን ይችላል፤ ዮሐ 15፥1-17 ይመ።

5፥2 *መጠበቂያ ማማ፤* በ1፥8 ላይ ከተገለጸው "ዳስ" ጋር ያነጻጽሩ። የእግዚአብሔር የወይን ቦታ ሁሉም ነገር ተሟልቶ የሚገኝበት ነው (ማቴ 21፥33 ይመ)። *የወይን መጭመቂያ፤* ተጨምቆ የሚወጣው የወይን ፈሳሽ የሚወርድበት ገንዳ ነው (16፥10 ይመ)። *ብሎ አሰበ፤ ነገር ግን፤* በትርጓሜው ተመሳሳይ አገላለጽ ጥቅም ላይ ውሏል (ቍ 7)።

5፥6 *ኵርንችትና እሾኽም፤* እነዚህ ቃላት በጥንድነት አምስት ጊዜ ተጠቅሰዋል (7፥23-25፤ 9፥18፤ 27፥4)። *እንዳይዘንብበት፤* ዝናብ መከልከሉ በምድሪቱ ላይ ርግማን መኖሩን ያሳያል፤ ዘዳ 28፥23-24፤ 2ሳሙ 1፥21፤ 1ነገ 17፥1 ይመ።

*5፥7* የወይኑ ቦታው መዝሙር እዚህ ላይ ተተርጕሞአል።

*5፥8-23፤* ስድስት ወዮዎች (ቍ 8፡11-12፡18-19፡20፡21፡22-23)። ሦስት የፍርድ ክፍሎችን (ቍ 9-10፤ 13-15፤ 24-25) በመከተል ተነግረዋል።

5፥8 *ቤትን በቤት ላይ ... መሬትን ከመሬት ጋር፤* በእስራኤል መሬት ይከራያል እንጂ አይሸጥም፤ ምክንያቱም መሬት ለእያንዳንዱ ቤተ ሰብ ተከፋፍሎ ተመድቦ ነበር (ዘኍ 27፥7-11፤ 1ነገ 21፥1-3 ይመ)።

5፥10 *አንድ የኢፍ መስፈሪያ፤* የጎሞር አንድ ዐሥረኛ ነው። ብዙ ጊዜ ከሕዝብ ኀጢአት የተነሣ የእህል ምርት በመጠንና በዐይነት ቀንሶ ይታያል (ዘዳ 28፥38-39፤ ሐጌ 2፥16-17 ይመ)። የወይኑና የእህሉ መጠን፣ ሩብ ጋሻ መሬት የወይን ተክል ቦታ ከሚሰጠውና አንድ ኆሞር የእህል ዘር ተዘርቶ ከሚገኘው ምርት እጅግ አነስተኛው መጠን ነው።

*5፥11-13፤* በስካርና በፈንጠዝያ የተሞላ ሕይወት ስለ መወገዙ አሞ 4፥1-3፤ 6፥6-7 ይመ።

[13]ስለዚህ ሕዝቤ
ዕውቀት በማጣቱ ይማረካል፤
መኳንንቱም በራብ ይሞታሉ፤
ሕዝቡም በውሃ ጥም ይቃጠላል።
[14]ስለዚህ ሲኦል[ሀ] ሆዷን አሰፋች፣
አፏንም ያለ ልክ ከፈተች፤
መኳንንቱና ሕዝቡ
ከረብሸኞቻቸውና ከጨፋሪዎቻቸው ጋር
ወደዚያ ይወርዳሉ።
[15]ሰው ይዋረዳል፤
የሰው ልጅም ዝቅ ዝቅ ይላል፤
የእብሪተኛውም ዐይን ይሰበራል።
[16]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ግን በፍትሕ
ከፍ ከፍ ይላል፤
ቅዱሱም አምላክ ቅድስናውን በጽድቅ
ይገልጻል።
[17]በጎችም በገዛ መሰማሪያቸው እንደሚሰማሩ
ሆነው ይግጣሉ፤
የበግ ጠቦቶችም በባለጠጎች ፍርስራሽ ላይ ሣር
ይበላሉ[ለ]።

[18]ኀጢአትን በማታለል ገመድ ለሚስቡ፣
በደልንም በሠረገላ ማሰሪያ ለሚጐትቱ
ወዮላቸው!
[19]በዐይናችን እንድናይ
እግዚአብሔር ይቸኵል፤
ሥራውንም ያፋጥን፤
የእስራኤልን ቅዱስ፣ የእርሱን ዕቅድ
እንድናውቃት ትቅረብ፤
ትምጣም ለሚሉ ወዮላቸው!"

[20]ክፉውን መልካም፣
መልካሙን ክፉ ለሚሉ
ብርሃኑን ጨለማ፣
ጨለማውን ብርሃን ለሚያደርጉ፣
ጣፋጩን መራራ፣
መራራውንም ጣፋጭ ለሚያደርጉ ወዮላቸው!

[21]ራሳቸውን እንደ ብልኅ ለሚቈጥሩ፣
በራሳቸውም አመለካከት ጥበበኛ ለሆኑ
ወዮላቸው!

[22]የወይን ጠጅ ለመጠጣት ጀግኖች፣
የሚያሰክር መጠጥ ለመደባለቅ ብርቱ ለሆኑ
ወዮላቸው!
[23]ጉቦን በመቀበል በደለኛን ንጹሕ ለሚያደርጉ፣
ለበደል አልባ ሰው ፍትሕን ለሚነፍጉ
ወዮላቸው!
[24]ስለዚህ የእሳት ነበልባል ገለባን እንደሚበላ፣
ድርቆሽም በእሳት ጋይቶ እንደሚጠፋ፣
የእነርሱም ሥር እንዲሁ ይበሰብሳል፤
አበባቸውም እንደ ትቢያ ይበናል፤
የሰራዊት ጌታ የእግዚአብሔርን ሕግ ንቀዋልና፤
የእስራኤል ቅዱስ የተናገረውንም ቃል
አቃለዋል።
[25]የእግዚአብሔር ቍጣ በሕዝቡ ላይ ነዶአል፤
እጁን አንሥቶ መቶአቸዋል፤

ተራሮች ራዱ፤
ሬሳዎችም በመንገድ ላይ እንደ ተጣለ ጥራጊ
ሆኑ፤
ይህ ሁሉ ሆኖ ግን ቍጣው ገና አልተመለሰም፤
እጁም እንደ ተነሣ ነው።

[26]ከሩቅ ያሉትን ሕዝቦች የሚጠራበትን ምልክት
ያቆማል፤
ከምድር ዳርቻም በፉጨት ይጠራቸዋል፤
እነርሱም እየተጣደፉ
በፍጥነት ይመጣሉ።
[27]በመካከላቸው ደካማና ስንኩል አይገኝም፤
የሚያንቀላፋና የሚተኛ አይኖርም፤
የወገባቸው መቀነት አይላላም፤
የጫማቸውም ማሰሪያ አይበጠስም።
[28]ፍላጻቸው የተሳለ፣
ቀስታቸውም የተደገነ ነው፤
የሠረገሎቻቸውም መንኰራኵሮች እንደ
ዐውሎ ነፋስ ናቸው።
[29]ጩኸታቸው እንደ አንበሳ ነው፤
እንደ አንበሳ ደቦል ያገሣሉ፤
ያደኑትንም ይዘው ይጮኻሉ፤
ተሸክመውት ይሄዳሉ፤ የሚያስጥልም የለም።
[30]በዚያን ቀን
እንደ ባሕር ሞገድ ይጮኹበታል፤
ማንም ወደ ምድር ቢመለከት፣

5፥13 ኢዮ22፥8፤ ምሳ10፥21፤ኢሳ1፥3፤ 3፥1፤49፥21
5፥14 ዘኍ16፥30፤ ምሳ30፥16፤ኢሳ22፥2፡ 13፤23፥7፤24፥8
5፥15 ኢሳ2፥9፡ 11፤10፥33
5፥16 ዘሌ10፥3፤ መዝ97፥9፤ኢሳ28፥17፤ 29፥23፤30፥18፤33፥5፡ 10፤61፥8፤ሕዝ36፥23
5፥17 ኢሳ7፥25፤ 17፥2፤32፥14፤ ሶፎ2፥6፡14
5፥18 ቍ8፤ ኢሳ59፥4-8፤ ኤር23፥14፤ሆሴ11፥4
5፥19 ኢሳ1፥4፤ 29፥23፤30፥11፡12፤ 60፥22፤ኤር17፥15፤ ሕዝ12፥22፤2ጴጥ3፥4
5፥20 ቍ8፤ ዘፍ18፥25፤1ነገ22፥8፤ ኢዮ24፥13፤ መዝ94፥21፤አሞ5፥7፤ ማቴ6፥22-23፤ ሉቃ11፥34-35
5፥21 ምሳ3፥7፤ ኢሳ47፥10፤ ሮሜ12፥16፤ 1ቆሮ3፥18-20
5፥22 1ሳሙ25፥36፤ ምሳ23፥20፤31፥4፤ ኢሳ22፥13፤65፥11፤ ኤር7፥18
5፥23 ቍ7፤ ዘፀ23፥8፤መዝ94፥21፤ ኢሳ1፥17፤10፥2፤ 29፥21፤59፥4፡13-15፤ ሕዝ22፥12፤አሞ5፥12፤ ያዕ5፥6
5፥24 2ነገ19፥30፤ ኢዮ6፥10፤18፥16፤ 24፥24፤መዝ107፥11፤ ኢሳ1፥4፡31፤8፥6፤ 10፥20፤12፥6፤30፥9፡ 12፤40፥8፤47፥14፤ ናሆ1፥10
5፥25 ዘፀ19፥18፤ 2ሳሙ22፥43፤ 2ነገ9፥37፤22፥13፤ ኢዮ40፥11፤ መዝ110፥6፤ኢሳ9፥12፡ 17፡21፤10፥4፡17፤ 26፥11፤31፥9፤ 66፥15፤ኤር4፥8፤ 6፥12፤ዳን9፥16
5፥26 ዘዳ28፥49፤ መዝ20፥5፤ኢሳ7፥18፤ 13፥5፤18፥3፤ዘካ10፥8
5፥27 ኢዮ12፥18፤ኢሳ14፥31፤22፥21፤40፥29-31፤ሕዝ23፥15፤ ኢዩ2፥7-8
5፥28 2ነገ2፥1፤ኢዮ1፥19፤39፥23፤መዝ7፥12፤ 45፥5፤ ሕዝ26፥11
5፥29 2ነገ17፥25፤ኢሳ10፥6፤42፥22፤49፥24-25፤ ኤር51፥38፤ሚክ5፥8፤ሶፎ3፥3፤ዘካ11፥3
5፥30 መሳ6፥2፤1ሳሙ2፥9፤ ኢዮ21፥30፤መዝ18፥28፤44፥19፤82፥5፤ 93፥3፤ኢሳ2፥11፤13፥10፤ 22፥5፤33፥2፤50፥3፤ኤር4፥23-28፤50፥42፤ ኢዩ2፥10፤ሉቃ21፥25

[ሀ]14 በዕብራይስጡ፣ *መቃብር* ማለት ነው።
[ለ]17 በዕብራይስጡ፣ *እንግዶች ይበሉታል* ይለዋል

5፥14 *ሲኦል፤* በሌላ ትርጕም፣ "መቃብር"፤ ተብሎአል፤ የዘፍ 37፥35 ማብ ይመ። መቃብር ምን ጊዜም ቢሆን አይጠግብም (ዕን 2፥5)።

*5፥18፤* በሆሴ 11፥4 ላይ፣ "በፍቅሬ ገመድ ሳብኋቸው" ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ።

*5፥19፤* "ይቸኵል"፣ "ያፋጥን" የሚሉት የዕብራይስጥ ቃላት "ማኸር፣ ሻላል-ሃሽ-ባዝ" በሚለው ስም ውስጥ ከመጀመሪያውና ከሦስተኛው ቃል ጋር ይመሳሰላሉ። ኢሳይያስም ለልጁ ይህን ስም ማውጣቱ (8፥3) በጊዜው የነበሩትን ኀጢአተኞች በአሽሙር ለመንካት ፈልጎ ያደረገው ሳይሆን እንዳልቀረ ይገመታል። በቍ 26 መሠረት እግዚአብሔር ፈጣን ፍርድ አምጥቶአል። *የእስራ ኤልን ቅዱስ፤* 11፥4 እና ማብ ይመ።

5፥22 *መጠጥ ለመደባለቅ፤* በወይን ጠጅና በብቅል መጠጥ ላይ ቅመማ ቅመሞች ይጨመር ነበር (ምሳ 23፥30 ይመ)።

*5፥23፤* 1፥23፤ 10፥1-2 ይመ።

5፥24 *የእስራኤል ቅዱስ ... አቃለዋል፤* ቍ 19፤ 1፥4 እና ማብ ይመ።

5፥25 *ተራሮች ራዱ፤* እግዚአብሔር ኀይሉን ሲገልጥ ተራ ሮች እንኳ ይንቀጠቀጣሉ (64፥3፤ ኤር 4፥24-26 ይመ)። ይህም እግዚአብሔር ራሱን የሚገልጥበትን ሁናቴ ለማሳየት የሚነገር የተለመደ አባባል ነው። *ገና ... እንደ ተነሣ ነው፤* ይህ አባባል በ9፥12፡17፡21፤ 10፥4 ላይ ተደጋግሞ ተገልጾአል።

5፥26 *ምልክት ያቆማል፤* ወታደሮችን ለመሰብሰብ (13፥2) እስራኤል ወደ አገሩ ይመለስ ዘንድ ሕዝቡን ለመጥራት ምልክት እንዲሆን ብዙውን ጊዜ በኰረብታ ላይ ዐርማ ተሰቅሎ ይውለበለብ ነበር። (11፥10፡12፤ 49፥22፤ 62፥10)። *ሩቅ ያሉትን ሕዝቦች፤* እስራ ኤልንና ይሁዳን በ722 እና በ701 ዓ.ቅ.ክ እንዳጠቃት እንደ አሦራ ውያንና በ605 ዓ.ቅ.ክ ወረራ እንደ ጀመሩት እንደ ባቢሎናውያን ያሉትን ማለት ነው። *ከምድር ዳርቻም፤* እንደ ግብፅና እንደ አሦር ያሉትን አገሮች ነው።

5፥27 *በመካከላቸው ደካማና ስንኩል አይገኝም፤* በ40፥29-31 ላይ ከተገለጸው ጋር ያነጻጽሩ።

5፥30 *በዚያን ቀን፤* የ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ።

ጨለማንና መከራን ያያል፤
ብርሃን እንኳ በደመናዎች ይጋረዳል።

## የኢሳይያስ ተልእኮ

**6** ንጉሥ ዖዝያን በሞተበት ዓመት እግዚአብሔርን ከፍ ባለና በከበረ ዙፋን ላይ ተቀምጦ አየሁት፤ የልብሱም ዘርፍ ቤተ መቅደሱን ሞልቶት ነበር። [2]ሱራፌልም ከእርሱ በላይ ቆመው ነበር፤ እያንዳንዳቸውም ስድስት ክንፍ ነበራቸው። በሁለት ክንፍ ፊታቸውን ይሸፍኑ ነበር፤ በሁለት ክንፍ እግራቸውን ይሸፍኑ ነበር፤ በሁለቱም ክንፍ ይበሩ ነበር፤ [3]እርስ በርሳቸው በመቀባበልም

"ቅዱስ፣ ቅዱስ፣ ቅዱስ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤
ምድር ሁሉ በክብሩ ተሞልታለች" ይሉ ነበር።

[4]ከድምፃቸው ጩኸት የተነሣ የመድረኩ መሠረት ተናወጠ፤ ቤተ መቅደሱም በጢስ ተሞላ። [5]እኔም፣ "ከንፈሮቼ የረከሱብኝ ሰው ነኝ፤ የምኖረውም ከንፈሮቹ በረከሱበት ሕዝብ መካከል ነው፤ ዐይኖቼም ንጉሡን፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔርን አይተዋልና ጠፍቻለሁ፣ ወዮልኝ!" አልሁ።

[6]ከዚያም ከሱራፌል አንዱ፣ ከመሠዊያው ላይ የእሳት ፍም በጕጠት ወስዶ፣ ወደ እኔ እየበረረ መጣ። [7]አፌንም በእሳቱ ነክቶ፣ "እነሆ፤ ይህ ከንፈሮችህን ነክቶአል፤ በደልህ ተወግዶልሃል፤ ኀጢአትህም ተሰርዮልሃል" አለኝ።

[8]ከዚያም የጌታ ድምፅ፣ "ማንን እልካለሁ? ማንስ ይሄድልናል?" ሲል ሰማሁት።

እኔም፣ "እነሆኝ፤ እኔን ላከኝ" አልሁ።

[9]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "ወደዚህ ሕዝብ ሂድ፤

"'መስማትን ትሰማላችሁ፤ ነገር ግን አታስተውሉም፤
ማየትንም ታያላችሁ፤ ነገር ግን ልብ አትሉም' ብለህ ንገራቸው።
[10]የዚህን ሕዝብ ልብ አደንድን፤
ጆሮአቸውን ድፈን፤
ዐይኖቻቸውንም ክደን፤
ይህ ካልሆነማ፣
በዐይናቸው አይተው፣ በጆሮአቸው ሰምተው፣
በልባቸውም አስተውለው
በመመለስ ይፈወሳሉ።"

[11]እኔም፣ "ጌታ ሆይ፤ ይህ የሚሆነው እስከ መቼ ነው?" አልሁት፤
እርሱም መልሶ እንዲህ አለኝ፤
"ከተሞች እስኪፈራርሱና፣
የሚኖሩባቸው እስኪያጡ፣

6፥1 ዘፀ24፥10፤ ዘኍ12፥8፤1ነገ22፥19፤ 2ነገ15፥7፤2ዜና26፥22፡23፤መዝ9፥4፤123፥1፤ ኢሳ52፥13፤53፥12፤ ዮሐ12፥41፤ራእ1፥13፤4፥2፤
6፥2 ሕዝ1፥5፡11፤ 10፥15፤ራእ4፥8
6፥3 ዘፀ15፥11፤ 16፥7፤ዘኍ14፥21፤ መዝ72፥19፤89፥8፤ ኢሳ11፥9፤54፥5፤ ሚል1፥11፤ራእ4፥8
6፥4 ዘፀ19፥18፤ 40፥34፤ሕዝ43፥5፤ 44፥4፤ራእ15፥8
6፥5 ዘፀ6፥12፤ 24፥10፤ዘኍ17፥12፤ ዘዳ5፥26፤ኢዮ42፥5፤ መዝ45፥3፤ኢሳ5፥8፤ 24፥23፤32፥1፤33፥17፤59፥3፤ኤር9፥3-8፤ 51፥57፤ሉቃ5፥8
6፥6 ዘሌ10፥1፤ ሕዝ10፥2
6፥7 ዘሌ26፥41፤ ኢሳ45፥25፤ኤር1፥9፤ ዳን10፥16፤12፥3፤ 1ዮሐ1፥7
6፥8 ዘፍ1፥26፤ 22፥1፤ዘፀ3፥4፤ ኢዮ40፥9፤ኤር26፥12፡15፤ሐሥ9፥4
6፥9 ኤር5፥21፤ ሕዝ3፥11፤አሞ7፥15፤ ማቴ13፥15፤28፥19፤ ሉቃ8፥10
6፥10 ዘፀ4፥21፤ ዘዳ29፥4፤ 32፥15፡39፤ መዝ119፥70፤ኢሳ29፥9፤42፥18-20፤43፥8፤44፥18፤ ሕዝ12፥2፤ማቴ13፥13-15፤ማር4፥12፤8፥18፤ዮሐ12፥40፤ ሐሥ28፥26-27
6፥11 ዘሌ26፥31፡ 43፤መዝ79፥1፡5፤ 109፥11፤ ኢሳ24፥10፤ኤር4፥13፤35፥17

***ጨለማንና መከራን፤*** የጦርነትን አሠቃቂነት ለመግለጽ በ8፥22 ላይ ተመሳሳይ የሆኑ ቃላት ገብተዋል።

6፥1 ***ንጉሥ ዖዝያን በሞተበት ዓመት፤*** ዘመኑ 740 ዓ.ቅ.ክ ነው። የኢሳይያስ ተልእኮ ከስብከት አገልግሎቱ ቀደም ብሎ ሳይጀምር እንዳልቀረ ይገመታል። ተከታታይ ንግሮቹን ከፍተኛ ደረጃ ላይ ለማድረስና በንግሮቹ ውስጥ አስደንጋጭ የፍርድ ቃላት ማረጋገጫ ለመስጠት የአገልግሎቱ ትረካ እዚህ ላይ ሲቀጥል አይታይም። ሕዝቡ፣ "የእስራኤልን ቅዱስ" ንቀውና አቃለው ነበር (5፥19)፤ አሁን ግን እግዚአብሔር ራሱ ኢሳይያስን በመላክ ስለ ጥፋታቸው እንዲያሳስባቸው አድርጎአል። ***ዖዝያን*** ከ792-749 ዓ.ቅ.ክ የገዛ፣ እግዚአብሔርን የሚፈራ ታላቅ ንጉሥ ነበር። ቤተ መቅደስ ገብቼ ዕጣን ማጠን አለብኝ ብሎ ቈርጦ በመነሣቱ ለምጽ ወጣበት፤ እስከ ሕይወቱ ፍጻሜም ለምጻም ነበር (2ዜና 26፥16-21)። ዓዛርያስ በመባልም ይጠራ ነበረ (2ነገ 14፥21፤ 2ዜና 26፥1)። ***እግዚአብሔርን፤*** እውነተኛው ንጉሥ (ቍ 5 ይመ)። ***ከፍ ባለና በከበረ፤*** በዕብራይስጡ ቅጅ 57፡15 ላይ እግዚአብሔር የሚለው ስም በሚገባበት ቦታ እነዚህ ቃሎች ገብተው ይገኛሉ፤ ሥቃይ ስለሚቀበለውም አገልጋይ ቃላቱ በ52፥13 ላይ ተጠቅሰዋል። ***የልብሱም ዘርፍ፤*** ረጅምና የተንዘረፈፈ ልብስ ነው፤ በራእ 1፥13 ላይ "የሰው ልጅ" ከለበሰው ልብስ ጋር ያነጻጽሩ። ***አየሁት፤*** በቤተ መቅደሱ ውስጥ በራእይ ሊሆን ይችላል። ***ቤተ መቅደሱን፤*** ከምድራዊው ቤተ መቅደስ ጋር ተቀራራቢ የሆነው ሰማያዊው ቤተ መቅደስ ሊሆን ይችላል። ዮሐንስ በራእዩ እግዚአብሔርን በዙፋኑ ላይ ተቀምጦ ያየበት ራእይም ከዚሁ ጋር ተመሳሳይ ነው (ራእ 4፥1-8)።

6፥2 ***ሱራፌልም፤*** ቍ 6 ይመ። በሌላ ስፍራ ያልተጠቀሱ መላእክት ናቸው። ለዚህ ቃል የተጠቀሰው የዕብራይስጡ ሥርወ ቃል "የተቃጠለ" የሚለውን ትርጒም ሲያሳይ፣ መላእክቱ የእግዚአብሔር አገልጋዮች እንደ መሆናቸው መጠን፣ ንጽሕናቸውን ለማመልከት የገባ ቃል፣ ሊሆን ይችላል። ቃሉ በ14፥29፤ 30፥6፤ ዘኍ 21፥6 ላይ ለተናዳፊ እባቦችም ተጠቅሶአል። በራእ 4፥6-9 ላይ እያንዳንዳቸው ስድስት ክንፍ ያላቸውን አርባዕቱ እንስሳትንም ያመለክታል። ***ፊታቸውን ይሸፍኑ ነበር፤*** የእግዚአብሔን ክብር ማየት አይቻላቸውምና።

6፥3 ***ቅዱስ፣ ቅዱስ፣ ቅዱስ፤*** ድግግሞሹ ወደር የሌለውን የእግዚአብሔርን ቅድስና በአጽንዖት ያመለክታል። በኤር 7፥4 ላይ፣ "የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ" የሚለው ቃል ሦስት ጊዜ መደጋገሙ፣ መቅደሱ በሕዝቡ መካከል ከመገኘቱ የተነሣ ኢየሩሳሌም በጠላት ልትደፈር አትችልም የሚል ጠንካራ እምነት በሕዝቡ ዘንድ መኖሩን በአጽንዖት ለማሳየት መሆኑን ያስተውሉ። ***በክብሩ ተሞልታለች፤*** በዘኍ 14፥21-22፤ መዝ 72፥18-19 በዓለም ሁሉ የሞላው የእግዚአብሔር ክብር በታምራታዊ ምልክቶች የታጀበ ነው።

6፥4 ***የመድረኩ ... ተናወጠ ... በጢስ ተሞላ፤*** የእግዚአብሔር የድምፁ ኀይል አስፈሪነት በተመሳሳይ ሁኔታ እስራኤላውያንን በሲና ተራራ እንዲንቀጠቀጡ አድርጎአቸዋል፤ ተራራውም በጢስ ተሸፍኖ ነበር (ዘፀ 19፥18-19፤ 20፥18-19 ይመ)።

6፥5 ***ዐይኖቼም ንጉሡን ... አይተዋልና፤*** እግዚአብሔርን ያየ ማናቸውም ሰው ወዲያውኑ እንደሚሞት ስለሚታሰብ፣ ኢሳይያስ ክፉኛ ፈርቶ ነበር (ዘፍ 16፥13፤ 32፥30 እና ማብ፤ ዘፀ 33፥20 ይመ)።

6፥6 ***የእሳት ፍም፤*** ኀጢአትን ለማስተስረይ መሥዋዕት በሚቀርብበት በማስተስረያ ቀን (ዘሌ 16፥12)፣ የእሳት ፍም ቅድስተ ቅዱሳን ይገባ ነበር፤ የ1፥25 ማብ ይመ።

6፥7 ***አፌንም በእሳቱ ነክቶ፤*** እግዚአብሔር ኤርምያስንም በላከው ጊዜ፣ አፉን በእጁ ዳሰታል (ኤር 1፥9)።

*6፥8-10፤* የኢሳይያስ የነቢይነት ተልእኮ ምፀታዊ የሆነ፣ ነገር ግን የዐመፀኛውን እስራኤል ጨካኝ ልብ የማደንደን ተገቢ ውጤት እና የማይቀረው ፍርድ ማስጠንቀቂያዎች አሉበት (ቍ 11-13 ይመ)፤ በተጨማሪም ኤር 1፥8፡19፤ ሕዝ 2፥3-4 ይመ።

6፥8 ***ይሄድልናል፤*** የሥላሴ ምክክር ነው፤ ኢሳይያስ እውነተኛ ነቢይ እንደ መሆኑ መጠን፣ እንደ ሚክያስ (1ነገ 22፥19-20) እና እንደ ኤርምያስ (23፥18፡22) የዚህ ምክክር ምስጢር ተገልጦለታል፤ ከዘፍ 1፥26፤ 11፥7፤ አሞ 3፥7 ጋር ያነጻጽሩ። ***እነሆኝ፤*** የዘፍ 22፥1 ማብ ይመ።

*6፥9-10፤* ክርስቶስ በዘሪው ምሳሌ ላይ ይህን ጠቅሶአል (ማቴ 13፥14-15፤ ማር 4፥12፤ ሉቃ 8፥10)፤ እንዲሁም ሮሜ 11፥7-10፡25 ይመ።

6፥10 ***ጆሮአቸውን ድፈን፤ ዐይኖቻቸውንም ክደን፤*** የእስራኤላውያን ደንቈርነትና ዕውርነት በ29፥9፤ 42፥18፤ 43፥8 ተጠቅሶአል፤ ይሁን እንጂ ይህ ሕዝብ አንድ ቀን ያያል፤ ይሰማልም (29፥18፤ 35፥5)።

ቤቶችም ወና እስኪሆኑና፣
ምድርም ፈጽሞ ባድማ እስክትሆን ድረስ፤
[12]እግዚአብሔርም ሰዎችን እስከሚያርቅ፣
ምድሪቱም ጨርሶ ባዶ እስክትሆን፣
[13]ከዐሥር አንድ ሰው እንኳ በምድሪቱ ቢቀር፣
እርሱም ደግሞ ይጠፋል፤
ነገር ግን የኮምብልና የወርካ ዛፍ በተቈረጠ
ጊዜ ጒቶ እንደሚቀር፣
ቅዱሱም ዘር
እንዲሁ በምድሪቱ ጒቶ ሆኖ ይቀራል።"

## የአማኑኤል ምልክትነት

**7** የዖዝያን የልጅ ልጅ፣ የኢዮአታም ልጅ አካዝ የይሁዳ ንጉሥ በነበረበት ዘመን፣ የሶርያ ንጉሥ ረአሶንና የእስራኤል ንጉሥ የሮሜልዩ ልጅ ፋቁሔ ኢየሩሳሌምን ሊወጉ ወጡ፤ ነገር ግን ድል ሊያደርጓት አልቻሉም።

[2]ለዳዊት ቤት፣ "ሶርያና ኤፍሬም ተባብረዋል" የሚል ወሬ በደረሰ ጊዜ፣ የዱር ዛፍ በነፋስ እንደሚናወጥ የአካዝና የሕዝቡ ልብ እንዲሁ ተናወጠ።

[3]እግዚአብሔርም ኢሳይያስን እንዲህ አለው፤ "አንተና ልጅህ ሸአር ያሹብ[+] አካዝን ለመገናኘት ወደ ልብስ አጣቢው ዕርሻ በሚወስደው መንገድ ወዳለው ወደ ላይኛው የኵሬ መስኖ ጫፍ ውጡ፤ [4]እንዲህም በለው፤ 'ተጠንቀቅ፤ ተረጋጋ፤ አትፍራ፤ በእነዚህ ከእሳት ተርፈው በሚጤሱት በሁለቱ የዕንጨት ጒማጆች፣ በሶርያና በንጉሥዋ በረአሶን እንዲሁም በሮሜልዩ ልጅ ቍጣ አትሸበር። [5]ሶርያ ኤፍሬምና፣ የሮሜልዩ ልጅ ሊያጠፉህ እንዲህ ብለው ተማከሩ፤ [6]"ይሁዳን እንውረር፤ እንበታትነው ተከፋፍለንም እንግዛው፤ የጣብኤልንም ልጅ እናንግሥባት።" [7]ልዑል እግዚአብሔር ግን እንዲህ ይላል፦

" 'ይህ ምክራቸው አይፈጸምም፤
ከቶም አይደረግም፤
[8]የሶርያ ራስ ደማስቆ፣
የደማስቆ ራስ ረአሶን ነውና፤
በሥልሳ አምስት ዓመት ውስጥ፣
የኤፍሬም ሕዝብ ይበታተናል፤ ሕዝብ
መሆኑም ይቀራል።
[9]የኤፍሬም ራስ ሰማርያ፣
የሰማርያም ራስ የሮሜልዩ ልጅ ነው።
እንግዲህ በእምነታችሁ ካልጸናችሁ፣
ፈጽሞ መቆም አትችሉም።' "

[10]እንደ ገናም እግዚአብሔር አካዝን እንዲህ አለው፤ [11]"ከጥልቁ ጥልቅ ወይም ከከፍታው ከፍታ ምልክት እንዲሰጥህ *ከእግዚአብሔር* ከአምላክህ ለምን።"

[12]አካዝ ግን፣ "አልለምንም፣ እግዚአብሔርንም አልፈታተንም" አለ። [13]ኢሳይያስም እንዲህ አለ፤ "እናንተ የዳዊት ቤት ሆይ፤ ስሙ፤ የሰውን ትዕግሥት መፈታተናችሁ አንሶ የአምላኬን ትዕግሥት ትፈታተናላችሁን? [14]ስለዚህ ጌታ ራሱ ምልክት ይሰጣችኋል፤ እነሆ፤ ድንግል ትፀንሳለች፤ ወንድ ልጅም ትወልዳለች፤ ስሙንም

6፥12 ዘዳ28፥64፤ ኢሳ5፥5:9፤60፥15፤ 62፥4፤ኤር4፥29፤ 30፥17
6፥13 ዘሌ27፥30፤ ዘዳ14፥2፤ኢዮ14፥7: 8፤ኢሳ1፥9፤5፥6፤ 10፥22
7፥1 ቍ5:8:9፤ 2ነገ15፥25:37፤ 1ዜና3፥13፤2ዜና28፥5፤ ኢሳ8፥6
7፥2 ቍ13፤ 2ሳሙ7፥11፤ኢሳ6፥4፤ 9፥9፤16፥5፤22፥22፤ ኤር21፥12፤ዳን5፥6፤ ሆሴ5፥3፤አሞ9፥11
7፥3 2ነገ18፥17፤ ኢሳ10፥21-22፤36፥2
7፥4 ዘፍ15፥1፤ ዘዳ3፥2፤20፥3፤ 2ነገ15፥27፤ኢሳ8፥12፤ 10፥24፤12፥2፤21፥4፤ 30፥15፤35፥4፤37፥6፤ 51፥13፤54፥14፤ ሰቆ3፥26፤አሞ4፥11፤ ዘካ3፥2፤ማቴ24፥6
7፥5 ቍ1:2
7፥7 መዝ2፥1፤ ኢሳ8፥10፤14፥24፤ 24፥3፤25፥8፤ 28፥16:18፤40፥8፤ 46፥10፤ሐሥ4፥25
7፥8 ቍ1፤ ዘፍ14፥15፤2ነገ17፥24፤ኢሳ8፥4፤9፥11፤ 17፥1-3
7፥9 2ነገ15፥29፤ 2ዜና20፥20፤ መዝ20፥8፤ኢሳ8፥6-8፡ 10፤9፥9፤28፥1:3፤ 30፥12-14፤40፥8
7፥11 ዘፀ7፥9፤ ዘዳ13፥2፤መዝ139፥8 7፥12 ዘዳ4፥34 7፥13 ቍ2፤ዘፍ30፥15፤ መዝ63፥1፤118፥28፤ኢሳ1፥14፤25፥1፤ 49፥4፤61፥10
7፥14 ዘፍ3፥15፤ 21፥22፤24፥43፤ዘፀ3፥12፤ኢሳ8፥8:10፤ማቴ1፥23፤ ሉቃ1፥31፤2፥12

[+]3 ሸአር ያሹብ ማለት፣ *ቅሬታዎች ይመለሳሉ* ማለት ነው

6፥12 *እስከሚያርቅ፤* 5፥13 ይመ።

6፥13 *ከዐሥር፤* የቀረውን የሚያመለክት ሲሆን፣ ይህም ቢሆን የሚጠፋ ነው። *ቅዱሱም ዘር፤* ታማኝ ሆነው በእስራኤል የተገኙትን እጅግ ጥቂቶቹን የሚመለከት ነው (ከ1ነገ 19፥18 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ1፥9 ማብ ይመ)። *ጒቶ፤* ሕዝብ ከዚህ ይወጣል፤ ለተመሳሳይ ዘይቤያዊ አባባል 11፥1 ይመ።

*7፥1-12፥6፤* ይህ በምዕራፍ 12 ላይ ባሉት የምስጋና መዝሙሮች አድኅ የሚታይ የኢሳይያስ ትንቢት ሁለተኛው ክፍል ነው።

*7፥1፤* ረአሶንና ፋቁሔ በ735 ወይም በ734 ዓ.ቅ.ክ ገደማ ያደረጉት ወረራ የሶርያና የኤፍሬም ጦርነት በመባል ይታወቃል። በስተ ምዕራብ በኩል ወዳሉት አገሮች ለመስፋፋት ጽኑ ፍላጎት የነበረውን የአሦርን ንጉሥ ለመጋፈጥ አካዝ እንዲተባበራቸው አራምና (ሶርያ) እስራኤል (ኤፍሬም፣ የቍ 2 ማብ ይመ) ሞክረው ነበር፤ ነገር ግን አልተሳካላቸውም። ኢሳይያስም አካዝ በዚህ ጦርነት እንዳይካፈል የመከላከል ሙከራ አድርጓል (2ነገ 16፥5-18፤ 2ዜና 28፥16-21 ይመ)። *ፋቁሔ፤* ከ752-732 ዓ.ቅ.ክ ገዛ (2ነገ 15፥27-31)።

7፥2 *ለዳዊት ቤት፤* ከዳዊት ዘር የሆነውን አካዝን ለማመልከት ነው (2ሳሙ 7፥8-11)። *ኤፍሬም፤* ሌላው የሰሜኑ መንግሥት የእስራኤል ስም ነው። *ልብ ... ተናወጠ፤* አካዝ ቀደም ብሎ በእስራኤልና በሶርያ ተሸንፎ ነበር (2ዜና 28፥5-8)።

7፥3 *ሸአር ያሹብ፤* የተረፉት አማራጭ ትርጒሙን ይመ። 10፥21-22። ለእያንዳንዱ ልጅ ትእምርታዊ ስም አውጥቶአል (8፥1:2:18)። *ወደ ላይኛው የኵሬ መስኖ፤* ስፍራው የት እንደ ሆነ በውል አይታወቅም። አካዝ በመስኖ ወደ ከተማዪቱ የሚገባውን ውሃ ማጠራቀሚያ ለማየት ሄዶ ይሆናል። *ልብስ አጣቢው ዕርሻ፤* በዚያን ጊዜ ልብስ የሚታጠበው በቀዝቃዛ ውሃ ውስጥ በመርገጥና ሳሙና ወይም ማጠቢያ ዱቄት በሚመስል ነገር በመጠቀም ነበር (ሚል 3፥2፤ ማር 9፥3 ይመ)።

7፥4 *በሁለቱ የዕንጨት ጒማጆች፤* የሶርያ ዋና ከተማ የሆነችው ደማስቆ 732 ዓ.ቅ.ክ በቴልጌልቴልፌልሶር ሠልሳዊ ተደምስሳ ነበር፤ እስራኤልም በዚሁ ዓመት ፈጽሞ ድል ሆና ነበር።

7፥6 *ጣብኤል፤* ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተ ምሥራቅ ካለው፣ "የጦብ ምድር" (መሳ 1፥3) ጋር የተያያዘ ሶርያዊ ስም ነው።

7፥8 *በሥልሳ አምስት ዓመት፤* 670 ዓ.ቅ.ክ አስራዶን፣ ከእርሱም በኋላ ጥቂት ቈይቶ አሹርባኒፓል የተባሉ የአሦር ነገሥታት በእስራኤል ቅኝ አገዛዝን መሠረቱ፤ ሳይማረኩ ከቀሩት ጥቂት እስራኤላውያን ጋር ያደረጉት ጋብቻም፣ "ለሳምራውያን" ወገን መፈጠር ምክንያት ሆነ (2ነገ 17፥24-34 እና የ2ነገ 17፥29 ማብ ይመ)፤ የኤፍሬምም ነገድ ራሱን እንደ ቻለ አንዳንድ ሕዝብ መታወቁ አበቃለት።

7፥9 *የሮሜልዩ ልጅ ነው፤* የዳዊትን ልጅ አካዝን ለመገዳደር ብቃት ያለው ሆኖ የተገኘው ፋቁሔ ብቻ ነበር። በሶርያና (ቍ 8) በእስራኤል (ቍ 9) ያሉት መሪዎች እንደ ሌላው ሰው ሁሉ ናቸው። በይሁዳ ግን መሪው ራሱ እግዚአብሔር ነው፤ እግዚአብሔር ራሱ ከእነርሱ ጋር ነውና (ቍ 14፤ 8፥8:10)። *በእምነታችሁ ካልጸናችሁ ... መቆም አትችሉም፤* የእግዚአብሔር ማስጠንቀቂያ እጅግ ከባድ መሆኑን ያመለክታል (1፥19-20፤ 25-26 እና ማብ ይመ)።

7፥11 *ምልክት፤* ይህ ምልክት ከጥቂት ዓመታት በኋላ ተፈጻሚ ሆኖአል፤ እግዚአብሔርም በዚህ ምልክት የአካዝን እምነት ለማጠናከር ፈቃደኛ ሆነ (ዘፀ 3፥12 ይመ)።

7፥13 *የዳዊት ቤት፤* የቍ 2 ማብ ይመ።

7፥14 *ምልክት፤* የቍ 11 ማብ ይመ (20፥3:37:30 ይመ፤ ከ8፥18 ጋር ያነጻጽሩ)። *ድንግል፤* የኢሳይያስ የመጀመሪያ ሚስቱ ሸአር ያሱብን ከወለደች በኋላ የሞተች ይመስላል፤ ስለዚህ ሁለተኛ ሚስቱ ልትሆን የታጨችውን ልጃገረድ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (8፥3)። በዘፍ 24፥43 ላይ ልታገባ የደረሰች ልጃገረድ በተመሳሳይ የዕብራይስጥ ቃል ተጠቅሳለች (ምሳ 30፥19)፤ ማቴ 1፥23 እዚህ ላይ የተጠቀሰችው ሴት የድንግል ማርያም ምሳሌ እንደ ሆነች ያረጋግጥልናል። *አማኑኤል፤* "እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ነው" የሚለው ስም አካዝ በጠላት በተከበበ ጊዜ እግዚአብሔር ከከበባው እንደሚያወጣው ተስፋ የሚሰጥ ቃል ነው፤

አማኑኤል[a] ብላ ትጠራዋለች። [15]ክፉውን መተውና መልካሙን መምረጥ ሲችል ቅቤና ማር ይበላል። [16]ነገር ግን ሕፃኑ ክፉውን መተውና መልካሙን መምረጥ ከመቻሉ በፊት የፈራሃቸው የሁለቱ ነገሥታት ምድር ባድማ ይሆናል። [17]ኤፍሬም ከይሁዳ ከተለየበት ቀን ጀምሮ እግዚአብሔር ከዚህ በፊት ታይቶ የማይታወቅ ዘመን በአንተ፣ በሕዝብህና በአባትህ ቤት ላይ ያመጣል፤ የሚያመጣውም የአሦርን ንጉሥ ነው።"

[18]በዚያን ቀን እግዚአብሔር ራቅ ካሉት ከግብፅ ወንዞች ዝንቦችን፣ ከአሦርም ምድር ንቦችን በፉጨት ይጠራል። [19]እነርሱም በሙሉ መጥተው፣ በየበረሓው ሸለቆ፣ በየዐለቱ ንቃቃት፣ በየእሾኹ ቍጥቋጦና በየውሃው ጕድጓድ ሁሉ ይሰፍራሉ። [20]በዚያን ቀን፣ እግዚአብሔር ከወንዝ[†] ማዶ በተከራየው ምላጭ፣ ማለትም በአሦር ንጉሥ፣ የራስና የእግር ጠጕራችሁን እንዲሁም ጢማችሁን ይላጫል። [21]በዚያን ቀን፣ አንድ ሰው አንዲት ጊደርና ሁለት በግ ብቻ ይተርፈዋል። [22]ከሚሰጡትም የተትረፈረፈ ወተት ቅቤ ይበላል፤ በምድሪቱም የቀሩ ሁሉ ቅቤና ማር ይበላሉ። [23]በዚያን ቀን ሺህ ሰቅል[‡] ብር የሚያወጣ አንድ ሺህ የወይን ተክል የነበረበት ቦታ ሁሉ፣ ኵርንችትና እሾኽ ብቻ ይሆናል። [24]ምድሪቱ በኵርንችትና በእሾኽ ስለምትሸፈን፣ ሰዎች ወደዚያ የሚገቡት ቀስትና ፍላጻ ይዘው ነው፤ [25]ኵርንችትና እሾኹን በመፍራት ከዚህ በፊት በመቈፈሪያ ተቈፍረው ወደ ነበሩት ወደ እነዚያ ኰረብ ታዎች ሁሉ ከእንግዲህ አትሄድም፤ ነገር ግን የከብቶች መሰማሪያና የበጎች መፈንጫ ቦታ ይሆናሉ።

7፥15 ቍ22፤ ዘፍ18፥8
7፥16 ዘዳ1፥39፤ 13፥16፤ኢሳ8፥4፤ 17፥3፤ኤር7፥15፤ ሆሴ5፥9፡13፤አሞ1፥3-5
7፥17 ቍ20፤ 1ነገ12፥16፤2ዜና28፥20
7፥18 ቍ20፡21፤ ኢሳ2፥11፤5፥26፤ 13፥5
7፥19 ቍ25፤ ኢሳ2፥19፤17፥9፤ 34፥13፤55፥13
7፥20 ቍ17፡18፤ ዘዳ28፥49፤ 2ሳሙ10፥4፤ 2ነገ18፥16፤ኢሳ8፥7፤ 10፥5፡15፤11፥15፤ 29፥16፤ኤር2፥18
7፥21 ቍ23፤ ኢሳ2፥17፤ኤር39፥10
7፥22 ቍ15፤ ዘፍ18፥8፤14፥30
7፥23 ቍ21፤ መሓ8፥11፤ኢሳ5፥6፤ ሆሴ2፥12
7፥24 ኢሳ5፥6
7፥25 ቍ19፤ ኢሳ5፥17፤ሐጌ1፥11
8፥1 ቍ3፤ ዘዳ27፥8፤ኢዮ19፥23፤ ኢሳ30፥8፤ኤር20፥3፤ 51፥60፤ሆሴ1፥4
8፥2 ቍ16፤ ኢሱ24፥22፤ሩት4፥9፤ 2ነገ16፥10፤ ኤር32፥10፡12፡25፡44
8፥3 ቍ1፤ዘፍ3፥15፤ ዘፀ15፥20

## አሦር የእግዚአብሔር መሣሪያ

**8** እግዚአብሔርም እንዲህ አለኝ፤ "ትልቅ ሰሌዳ ወስደህ፣ 'ማኼር-ሻላል-ሃሽ-ባዝ'[1] ብለህ በተለመደው በሰው ፊደል ጻፍበት። [2]እኔም፣ ካህኑን ኦሪያንንና የበራክዩን ልጅ ዘካርያስን ታማኝ ምስክሮቼ እንዲሆኑ እጠራቸዋለሁ።"

[3]እኔም ወደ ነቢዪቱ ሄድሁ፤ እርሷም ፀነሰች፤ ወንድ ልጅም ወለደች። እግዚአብሔርም እንዲህ አለኝ፤ "ስሙን ማኼር-ሻላል-ሃሽ-ባዝ ብለህ ጥራው። [4]ሕፃኑም፣ 'አባባ' ወይም 'እማማ' ብሎ መጥራት ከመቻሉ በፊት፣ የደማስቆ ሀብትና የሰማርያ ምርኮ በአሦር ንጉሥ ይወሰዳል።"

[5]እግዚአብሔርም እንደ ገና እንዲህ ሲል
ተናገረኝ፤
[6]"ይህ ሕዝብ በጸጥታ የሚፈሰውን
የሰሊሆምን ውሆች ትቶ፣
በረአሶንና
በሮሜልዩ ልጅ ተደስቶአልና።

8፥4 ዘፍ1415፤ኢሳ7፥8፡16 8፥6 ነህ3፥15፤ኢሳ5፥24፤7፥1፤ዮሐ9፥7

[a]14 *አማኑኤል* ማለት፣ *እግዚአብሔር ከእኛ ጋር* ማለት ነው።
[†]20 የኤፍራጥስ ወንዝ ነው።
[‡]23 11.5 ኪሎ ግራም ያህል ነው።
[1]1 በዚህና በቍጥር 3 ላይ፣ *ማኼር-ሻላል-ሃሽ-ባዝ* ማለት፣ *ምርኮ ፈጠነ፤ብዝበዛ ቸኰለ* ማለት ነው።

ዘኍ 14፥9፤ 2ዜና 13፥12፤ መዝ 46፥7 ይመ። "አማኑኤል" የሚለው ስም በ8፥8፡10 ላይ እንደ ገና ተጽፎ እናገኘዋለን፤ የማኼር ሻላል ሃሽ ባዝ (8፥3) ሌላ ስምም ሊሆን ይችላል። ይህ ከሆነ ደግሞ የኢሳይያስ ልጅ ስም በተጨማሪ ሌላ ትልቅ ቁም ነገር የያዘ ትርጕም አለው ማለት ነው (የ8፥3 ማብ ይመ)። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የዚህ ትንቢት ፍጻሜ ነው፤ "እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ነው" የሚለው ትርጕም የተፈጸመው በእርሱ ነውና (ማቴ 1፥23 ከኢሳ 9፥6-7 ጋር ያነጻጽሩ)።

7፥15 *ክፉውን ... መልካሙን መምረጥ ሲችል፤* ይህ በሙሴ ሕግ መሠረት ግብረ ገባዊ ግዴታንና ኀላፊነትን ለመወጣት የሚያስችል የዕድሜ ክልል እንዳለ የሚያሳይ ሲሆን፣ ይኸውም 12 ወይም 13 ዓመት ነው። ስለዚህ ይህ ልጅ ዕድሜው 12 ወይም 13 ሲሆን (722 ወይም 721 ዓ.ቅ.ክ ላይ) አሦራውያን እስራኤልን ስለ ደመሰሱና አዝመራው በሙሉ ስለ ወደመ፣ ቅቤና ማር ሊበላ ችሉአል። አንዳንዶች ይህ አባባል አጭር ጊዜን እንደሚ ያካትት፤ በቍ 16 እና በ8፥4 ላይ ካለው ጋርም አንድ ዐይነት እንደ ሆነ ያምናሉ። *ቅቤና ማር፤* ይህን ምግብ መብላት ከምድሪቱ የወጡ ሰዎች ወደ ሚመገቡት ቀለል ያለ ምግብ መመለስን ያመለክታል። የአሦራውያን ወረራ በገጠሩ ክፍል ላይ ጕዳት አስከትሉአል፤ ዕርሻም እንዳይታረስ አድርጎአል (ከቍ 22-25 ይመ)።

7፥16 *ሕፃኑ ... መምረጥ ከመቻሉ በፊት ... ምድር ባድማ ይሆናል፤* የቍ 4 ማብ ይመ፤ ከ8፥4 ጋር ያነጻጽሩ። የልጁ ዕድሜ 12 ወይም 13 ከመሆኑ በፊት ሶርያና እስራኤል ባድማ ይሆናሉ። ይህ የሆነው 732 ዓ.ቅ.ክ የልጁ ዕድሜ ሁለት ዓመት ያህል ሲሆነው ነው።

7፥17 *ኤፍሬም ከይሁዳ ከተለየበት ቀን ጀምሮ፤* ከሁለት ምእት ዓመት በፊት (1ነገ 12፥19-20 ይመ)። *የአሦርን ንጉሥ፤* አካዝ የአሦርን ንጉሥ መጠጋቱ ጊዜያዊ ሰላም አምጥቶለት ይሆናል (2ነገ 16፥8-9)፤ የኋላ ኋላ ግን አሦር ይሁዳን ወራለች (8፥7-8፤ 36፥1 ይመ)።

7፥18፡20፡23 *በዚያን ቀን፤* ችግሮቻቸው፣ "የእግዚአብሔርን ቀን" ከወዲሁ የሚለማመዱባቸው ይሆናሉ (የ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ)።

7፥18 *ዝንቦችን ... ንቦችን፤* ዘፀ 23፥28 እና ማብ ይመ።

7፥19 *በየዐለቱ ንቃቃት፤* የ2፥10 ማብ ይመ። ከወራሪዎች ማምለጥ እንደማይቻል ያመለክታል።

7፥20 *ጠጕራችሁን ... ጢማችሁን ይላጫል፤* ጢምን ተገዶ መላጨት እንደ ትልቅ ውርደት ይቈጠራል (2ሳሙ 10፥4-5)። በሐዘን ጊዜ ግን የራስ ጠጕርንና ጢምን መላጨት የተለመደ ነው (15፥2፤ የ3፥17 ማብ ይመ)።

7፥23 *ኵርንችትና እሾኽ፤* የ5፥6 ማብ ይመ። የወይን ተክሉ ቦታና የዕርሻው መሬት ሁሉ መጥፋት የ5፥5-6 ትንቢት ፍጻሜ ነው።

8፥1-2 *ሰሌዳ ...ምስክሮቼ፤* እነዚህ ምስክሮች የኢሳይያስን ጋብቻ (የ7፥14 ማብ ይመ) ወይም ከማኼር ሻላል ሃሽ ባዝ ጋር የተያያዘውን የምልክት ድርጊት ሕጋዊነት የሚያረጋግጡ ናቸው። "ሰሌዳ" የሚለው የዕብራይስጡ ቃል፣ "የተከፈተው የውል ወረቀት" ከሚለው ከኤርምያስ 32፥11 ጋር ተዛማጅነት አለው።

8፥2 *ካህኑን ኦሪያንን፤* በአካዝ ዘመን ሲያገለግል የነበረ ነው (2ነገ 16፥10-11 ይመ)።

*8፥3-10፤* 7፥14-17 ይመ።

8፥3 *ነቢዪቱ ... ወንድ ልጅ፤* ምናልባት የ7፥14 የመጀመሪያ ፍጻሜ ነው። ነቢዪቱ ነቢዩን ያገባችበት ብቸኛ ምክንያት ነው (የዘፀ 15፥20 ማብ ይመ)። ይሁዳ እንጂ ወጣቷ ሴት ነቢዩን አግብታ ስለ ነበር ነቢዪት ተብላ ይሆናል። *ማኼር - ሻላል- ሃሽ- ባዝ፤* ይህ ትእምርታዊ ስም፣ የአካዝ ጠላቶች እንደሚበዘበዙ ያመለክታል (ቍ 4 እና የ7፥4 ማብ ይመ)፣ ይሁን እንጂ ይሁዳ እንደሚሠቃይም ያሳያል (ቍ 7-8 ይመ)።

8፥4 *ከመቻሉ፤* ሁለት ዓመት ገደማ ሲሆነው፤ ይህ ጊዜ በ7፥16 ከተገለጸው ጋር አንድ ነው (የ7፥4፡16 ማብ ይመ)። *የሰማርያ ምርኮ በአሦር ... ይወሰዳል፤* ይህ እስከ 722-721 ዓ.ቅ.ክ ድረስ ያልተፈጸመው (የ7፥15 ማብ ይመ) የሰሜኑ መንግሥት መደምሰስ የመጀመሪያ ደረጃ ነው (የ7፥4 ማብ ይመ)።

8፥6 *የሰሊሆምን ውሆች፤* የኢየሩሳሌም ውሃ ከግዮን ምንጭ (2ዜና 32፥30) ወደ ሰሊሆም መጠመቂያ ይፈስ ነበር (ዮሐ 9፥7 ይመ)፤ ይህ የሚያመለክተው ፈሳሹን ውሃ ሲሆን፣ የእግዚአብሔርን የጥበቃ ኀይል በምሳሌነት ያሳያል (ነህ 3፥15)። *በረአሶንና በሮሜልዩ ልጅ፤* ረአሶንና ፋቁሔ በ732 ዓ.ቅ.ክ ሞተዋል (2ነገ16፥9፤ የኢሳ 7፥1 ማብ ይመ)።

[7]ስለዚህ ጌታ ታላቁንና ብርቱውን የጐርፍ ውሃ[ነ]
የአሦርን ንጉሥ ከነግርማ ሞገሱ ሁሉ ያመጣባቸዋል::
ውሃውም ከቦዩ ዐልፎ ተርፎ
በወንዙ ዳር ያለውን ምድር ሁሉ ያጥለቀልቃል፤
[8]እየጠራረገ ወደ ይሁዳ ይወርዳል፤
እያጥለቀለቀ ያልፋል፤
እስከ ዐንገትም ይደርሳል፤
አማኑኤል[ፐ] ሆይ፤
የተዘረጉ ክንፎቹ ምድርህን ከዳር እስከ ዳር ይሸፍናሉ::"

[9]እናንተ አሕዛብ፣ ፎክሩ[ኦ]፤
ግን ደንግጡ::
በሩቅ አገር ያላችሁ አድምጡ፤
ለጦርነትም ተዘጋጁ፤ ነገር ግን ደንግጡ፤
ለጦርነትም ተዘጋጁ፤ ነገር ግን ደንግጡ፤
[10]ተመካከሩ፤ ግን አይሳካም፤
ዕቅድ አውጡ፤ ሆኖም አይጸናም፤
እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ነውና::[ከ]

## እግዚአብሔርን ፍሩ

[11]እግዚአብሔር ብርቱ እጁን በላዬ አድርጎ የእነዚህን ሰዎች መንገድ እንዳልከተል አስጠ ነቀቀኝ፤ እንዲህም አለኝ፤

[12]"እነዚህ ሰዎች፣ 'አድማ' ብለው የሚጠሩትን፣
ማንኛውንም ነገር፣ 'አድማ' አትበሉ፤[ኸ]
እነርሱ የሚፈሩትን አትፍሩ፤
አትሸበሩለትም::
[13]ልትቀድሱ የሚገባው የሰራዊት ጌታ እግዚ አብሔርን ብቻ ነው፤
ልትፈሩት የሚገባው እርሱን ነው፤
ልትንቀጠቀጡለት የሚገባውም እርሱ ነው::
[14]እርሱም መቅደስ ይሆናል፤
ለሁለቱ የእስራኤል ቤት ግን
የሚያደናቅፍ ድንጋይ
የሚያሰናክልም ዐለት ይሆንባቸዋል፤
ለኢየሩሳሌም ሕዝብም
ወጥመድና አሽክላ ይሆናል::
[15]ከእነርሱ ብዙዎች ይሰናከላሉ፤
ይወድቃሉ፤ ይሰበራሉ፤
ወጥመድ ይገባሉ፤ ይያዛሉም::"

[16]ምስክርነቱን እሽገው፤
ሕጉንም በደቀ መዛሙርቴ መካከል አትመው::
[17]ፊቱን ከያዕቆብ ቤት የሸሸገውን
እግዚአብሔርን እጠብቃለሁ፤
እርሱንም ተስፋ አደርጋለሁ::

[18]እነሆ፤ እኔና እግዚአብሔር የሰጠኝ ልጆች በጽዮን ተራራ ከሚኖረው ከሰራዊት ጌታ ከእግዚአብሔር ለእስራኤል ምልክትና ድንቅ ነን::

[19]ሰዎች፣ "የሚያነበንቡትንና የሚያሾካሹኩትን ሟርተኞችንና መናፍስት ጠሪዎችን ጠይቁ ቢሏችሁ፣ ሕዝቡ አምላኩን መጠየቅ አይገ ባውምን? በሕያዋን ምትክ ሙታንን መጠየቅ ለምን አስፈለገ? [20]ወደ ሕጉና ወደ ምስክር ቃሉ ሂዱ! እነርሱም እንዲህ ያለውን ቃል ባይ ናገሩ የንጋት ብርሃን አይበራላቸውም:: [21]ተጨን ቀውና ተርበው በምድሪቱ ላይ ይንከራተታሉ፤ ክፉኛ ሲራቡም ይቈጣሉ፤ ወደ ላይ እየተ መለከቱ ንጉሣቸውንና አምላካቸውን ይራገ

8፥7 ኢሱ3፥15፤ 2ዜና28፥20፤ኢሳ7፥20፤ 10፥16፤17፥12-13፤ 28፥2:17፤30፥28፤ 43፥2፤ዳን11፥40፤ ናሆ1፥8
8፥8 ኢሳ7፥14፤ 18፥6፤28፥15፤46፥11፤ ኤር4፥13፤48፥40
8፥9 ኢሱ6፥5፤ ኢዮ34፥24፤ ኢሳ17፥12-13፤ ኤር6፥4፤46፥3፤ 51፥12:27-28፤ ሕዝ38፥7፤ኢዩ3፥9፤ ዘካ14፥2-3
8፥10 ኢዮ5፥12፤ ምሳ19፥21፤21፥30፤ ኢሳ7፥7:14፤ ማቴ1፥23፤ሮሜ8፥31
8፥11 ሕዝ1፥3፤ 2፥8፤3፥14
8፥12 ኢሳ7፥2:4፤ 20፥5፤30፥1፤36፥6፤ ማቴ10፥28፤ 1ጴጥ3፥14
8፥13 ዘፀ20፥20፤ ዘኍ20፥12፤ኢሳ29፥23
8፥14 መዝ118፥22፤ 119፥110፤ኢሳ4፥6፤ 24፥17-18፤ኤር6፥21፤ ሕዝ3፥20፤14፥3:7፤ ሉቃ2፥34፤20፥18፤ ሮሜ9፥33፤1ጴጥ2፥8
8፥15 ምሳ4፥19፤ ኢሳ28፥13፤59፥10፤ ሮሜ9፥32
8፥16 ሩት4፥7፤ ኢሳ29፥11-12፤ ኤር32፥14፤ዳን8፥26፤ 12፥4
8፥17 ዘዳ31፥17፤ መዝ22፥5፤27፥14፤ ዕብ2፥13
8፥18 ዘፍ33፥5፤ ዘፀ3፥12፤ዘዳ28፥46፤ መዝ9፥11፤ሕዝ4፥3፤ 12፥6:11፤24፥24፤ ሉቃ2፥34፤ዕብ2፥13
8፥19 ዘሌ19፥31፤ ዘኍ27፥21፤1ሳሙ28፥8፤ኢሳ29፥4 8፥20 ቍ22፤ሩት4፥7፤ኢሳ1፥10፤ 9፥2፤59፥9፤60፥2፤ ሚክ3፥6፤ሉቃ16፥29
8፥21 ዘፀ22፥28፤ኢዮ18፥12፤ 30፥3፤ራእ16፥11

[ነ]7 የኤፍራጥስ ወንዝ ነው::
[ፐ]8 *አማኑኤል* ማለት፣ *እግዚአብሔር ከእኛ ጋር* ማለት ነው:
[ኦ]9 ወይም፣ *የከፋውን ነገር አድርጉ*
[ከ]10 ዕብራይስጡ፣ *አማኑኤል* ይላል::
[ኸ]12 ወይም *ለሴማግንት አትተፉ እነዚህ ሰዎች ሁል ጊዜ ለሴማግንት ይጠራሉ*

8፥7-8 *ታላቁንና ብርቱውን የጐርፍ ውሃ ... እየጠራረገ፤* አብዛኛውን ጊዜ ታላላቅ ወንዞች ኀይለኛ ወራሪ ሰራዊትን ያመለ ክታሉ (28፥17-19 ይመ)::

8፥8 *እስከ ዐንገትም፤* 701 ዓ.ቅ.ክ ላይ የተጀመረው የሰናክሬም ወረራ፣ ከኢየሩሳሌም በቀር የይሁዳን ከተሞች በሙሉ አጥለቅልቆ ነበር (1፥7-9 ይመ):: *የተዘረጉ ክንፎቹ፤* አገላለጹ በፍጥነት የታወቀውን ንስር የሚያመለክት ነው:: *አማኑኤል፤* ሁሉም የጠፋ ይመስላል፤ ይሁን እንጂ፣ "እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ነው" (ቍ 10) ጠላትንም ያሸንፋል (የ7፥14 ማብ ይመ)::

8፥9 *አሕዛብ ... ደንግጡ፤* ሶርያና እስራኤል ተሸንፈው እንደሚደመሰሱ (7፥7-9)፣ አሦርና ባቢሎንም በመጨረሻ ይወድቃሉ::

8፥10 *አይጸናም፤* እስከ መጨረሻ የሚጸናው የእግዚአብሔር ዐላ ማና ዕቅድ ብቻ ነው::

*8፥11 ብርቱ እጁን በላዬ፤* ሕዝ 1፥3፤ 37፥1፤ 40፥1 ይመ:: ነቢያት እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር መሆኑንና ሕይወታቸውንም እንደሚቈጣጠር ያውቃሉ::

*8፥12 አድማ፤* ሕዝቡና መንግሥቱ በአሦር እንዳይደገፍ ኢሳይያስ የሰጠው ማስጠንቀቂያ እንደ ሤራ ተቈጥሮ ነበር (የ7፥1 ማብ ይመ ከኤር 37፥13-14 ጋር ያነጻጽሩ)::

8፥13 *ልትፈሩት የሚገባው፤* 7፥2፤ ምሳ 1፥7 ይመ::

8፥14 *መቅደስ ... ድንጋይ የሚያሰናክልም ዐለት፤* ጌታ የሕ ይወታችን የማእዘን ደንጋይ ወይም መሰናከያ ዐለት ነው (28፥16 ይመ):: ይህን ሐሳብ ስለ ጌታ ከተነገረው ጋር ለማገናዘብ ሮሜ 9፥33፣ 1ጴጥ 2፥6-8 ይመ:: *ለሁለቱ፤* የሰሜኑና የደቡቡ መንግሥታት፣ እስራኤልና ይሁዳ ናቸው::

*8፥16፤* ምናልባት ከቍ 1-2 ጋር የሚዛመደውን የሕግ ሐሳብ ያመለክታል (ማብ ይመ):: *ምስክርነቱን፤* ቍ 20 ይመ፤ ኢሳይያስ ያስተማረውን ትምህርት ማለት፣ "ሕጉን" በማስታወስ ትንቢቱ እውነት መሆኑን ደቀ መዛሙርቱ በኋላ ማረጋገጥ ይችላሉ፤ ቃሉ ከዚህ ሌላ የሚገኘው በሩት 4፥7 ላይ ብቻ ነው:: *ሕጉንም፤* በዕብ ራይስጥ፣ "ትምህርት" ወይም "መመሪያ" ተብሎ መተርጐም ይችላል:: አሦርን በተመለከተ ኢሳይያስ ያስተማረው የሕግ ትምህርትና የአሦርን ወረራ የሚገልጠው ጽሑፍ ተሰባስቦና ታትሞ ለተከታዮቹ ተሰጥቶ ነበር፤ እነርሱም እግዚአብሔር እውን አድርጎት እስከ ተፈ ጸመበት ጊዜ ድረስ ጠብቀው አቈይተውታል (ኤር 32፥12-14:44 ይመ)::

*8፥17-18፤* በዕብ 2፥13 ላይ እነዚህ ጥቅሶች ክርስቶስን በማመልከት ተጠቅሰዋል::

8፥17 *ፊቱን ... የሸሸገውን፤* 1፥15፤59፥2፤ ሚክ 3፥4 ይመ::

8፥18 *ምልክትና ድንቅ፤* የ7፥3:14 ማብ ይመ፤ ከ20፥3 ጋር ያነጻጽሩ::

8፥19 *ሟርተኞችንና ... መናፍስት ጠሪዎችን፤* ሕዝቡ በየጊዜው ካጋጠመው ችግር የተነሣ ንጉሥ ሳኦል ከሳሙኤል መንፈስ (1ሳሙ 28፥8-11) ጋር ለመነጋገርና ስለ ወደፊቱም ለማወቅ እንዳ ደረገው፣ ወደ ሙታን መንፈስ ዘወር ብሏል የ3፥2-3 ማብ ይመ::

8፥20 *ወደ ሕጉና ወደ ምስክር ቃሉ፤* ቍ 16 እና ማብ ይመ፤ እግዚአብሔር በኢሳይያስ አማካይነት የተናገረውን፣ እንደ ገናም ኢሳይያስና ልጆቹ የገለጹትን፣ በ"ድንቅና ምልክት (ቍ 18) የተደገፈውን የእግዚአብሔር ቃል በመከተል ብቻ የእስራኤል የንጋት ብርሃን ይወጣል::

*8፥21-22፤* የአሦር ወረራ በመላው እስራኤል ጥልቅ ሐዘን አስከትሎ ነበር::

8፥21 *ንጉሣቸውንና አምላካቸውን ይራገማሉ፤* ይህን የሚያደርጉት ከደረሰባቸው ሥቃይ የተነሣ ነው (ከምሳ 19፥3 ጋር ያነጻጽሩ)፣

ማሉ። [22]ከዚያም ወደ ምድር ይመለከታሉ፣ የሚያዩትም ጭንቀት፣ ጨለማና የሚያስፈ ራም ጭጋግ ብቻ ነው፤ ወደ ድቅድቅ ጨለ ማም ይጣላሉ።

## ሕፃን ተወለደልን

**9** ነገር ግን ተጨንቀው የነበሩ ከእንግዲህ ተስፋ ቢስ አይሆኑም። በቀደመው ዘመን የዛብሎንንና የንፍታሌምን ምድር አዋረደ፤ በሚመጣው ዘመን ግን ከዮርዳኖስ ማዶ፣ በባሕር መንገድ አጠገብ ያለውን የአሕዛብን ገሊላ ያከብራል፤

[2]በጨለማ የሚኖር ሕዝብ
  ታላቅ ብርሃን አየ፤
በሞት ጥላ[*] ምድር ለኖሩትም
  ብርሃን ወጣላቸው።
[3]ሕዝብን አበዛህ፤
  ደስታቸውንም ጨመርህ፤
ሰዎች ምርትን ሲሰበስቡ፣
  ምርኮንም ሲከፋፈሉ
ደስ እንደሚላቸው ሁሉ፣
  እነርሱም በፊትህ ደስ ይላቸዋል።
[4]ምድያም ድል በተመታ ጊዜ እንደ ሆነው፣
  የከበዳቸውን ቀንበር፣
በትከሻቸው ላይ የነበረውን በትር፣
  የተጨቈኑበትንም ዘንግ ሰብረህላቸዋል።
[5]የጦረኞች ጫማ ሁሉ፣
  በደም የተለወሰ ልብስም ሁሉ፣
ለእሳት ይዳረጋል፤
  ይማገዳልም።
[6]ሕፃን ተወልዶልናልና፤
  ወንድ ልጅ ተሰጥቶናል፤
አለቅነትም በጫንቃው ላይ ይሆናል።
  ስሙም፣
ድንቅ መካር፣[°] ኀያል አምላክ፣
  የዘላለም አባት፣ የሰላም ልዑል ይባላል።
[7]ለመንግሥቱ ስፋት፣
  ለሰላሙም ብዛት ፍጻሜ የለውም፤
ከአሁን ጀምሮ እስከ ዘላለም፣
  መንግሥቱን በፍትሕና በጽድቅ ይመሠርታል፤
ደግፎ በመያዝም ያጸናዋል።
  በዳዊት ዙፋን ይቀመጣል፤
አገሩንም ሁሉ ይገዛል፤
  የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ቅናት
  ይህን ያደርጋል።

## የእግዚአብሔር ቍጣ በእስራኤል ላይ

[8]ጌታ በያዕቆብ ላይ ቃል ላከ፤
  በእስራኤልም ላይ ይወድቃል።
[9]ሕዝቡ በሙሉ፣
  ኤፍሬምና የሰማርያ ነዋሪዎች
ይህን ያውቃሉ፤
  በትዕቢትና በልብ እብሪትም እንዲህ
    ይላሉ፤
[10]"ጡቦቹ ወድቀዋል፤
  እኛ ግን በጥርብ ድንጋይ መልሰን እንገነባለን፤
የሾላ ዛፎቹ ተቈርጠዋል፤
  እኛ ግን በዝግባ እንተካለን።"
[11]ነገር ግን እግዚአብሔር የረአሶንን ጠላቶች
    ያጠናክራል፤
  በእነርሱም ላይ ያመጣባቸዋል፤
  ባለጋራዎቻቸውንም ያነሣሣባቸዋል።
[12]ሶርያውያን ከምሥራቅ፣ ፍልስጥኤማውያን
    ከምዕራብ፤
  አፋቸውን ከፍተው እስራኤልን ይበሉ
    ጧታል።

ይህም ሁሉ ሆኖ፣ ቍጣው ገና አልበረደም፤
  እጁ እንደ ተዘረጋ ነው።

8፥22 ቍ 20፤ ኢዮ3፥13፤15፥24፤ ኢሳ5፥30፤ኢል2፥2፤ ማቴ25፥30፤ ራእ16፥10
9፥1 2ነገ15፥29፤ ኢዮ15፥24
9፥2 መዝ36፥9፤ 82፥5፤107፥10፡14፤ ኢሳ8፥20፤42፥6፤ 49፥6፤58፥8፤60፥19፤ ሚል4፥2፤ ማቴ4፥15-16፤ ሉቃ1፥79፤ኤፌ5፥8
9፥3 ዘፀ15፥9፤ ኢሱ22፥8፤ ኢዮ12፥23፤መዝ4፥7፤ 119፥162፤ኢሳ25፥9
9፥4 መሳ7፥25፤ ኢዮ34፥24፤መዝ81፥6፤ ኢሳ10፥27፤14፥4፡25፤ 16፥4፤29፥5፡20፤ 37፥36-38፤49፥26፤ 51፥13፤54፥14፤ 58፥6፡9፤60፥18፤ ኤር2፥20፤30፥8፤ ሕዝ30፥18፤ናሆ1፥13፤ ማቴ11፥30
9፥5 ኢሳ2፥4
9፥6 ዘፍ3፥15፤ ዘፀ4፥22፤ዘዳ7፥21፤ ኢዮ15፥8፤መዝ24፥8፤ 90፥2፤ኢሳ10፥21፤ 11፥2፤22፥22፤ 26፥3፡12፤28፥29፤ 42፥13፤53፥2፡5፤ 64፥8፤66፥12፤ ኤር33፥6፤ሚክ5፥5፤ ማቴ28፥18፤ሉቃ2፥1 1፡14፤ዮሐ3፥16፤ 14፥9-10
9፥7 2ሳሙ7፥13፤ 2ነገ19፥31፤ መዝ72፥2፤85፥8፤ 119፥165፤ኢሳ1፥26፤ 2፥4፤ 11፥4፡9፤16፥5፤ 26፥3፡11፡12፤32፥1፡ 16፡17፤33፥5፤37፥32፤ 42፥1፡13፤48፥18፤ 59፥17፤60፥17፤ 63፥15፤ኤር23፥5፤ 33፥14፤ዳን2፥44፤ 4፥3፤ሉቃ1፥33፤ ዮሐ12፥34፤ 1ቆሮ15፥25
9፥8 ዘዳ32፥2
9፥9 ኢሳ7፥2፡9፤ 46፥12፤48፥4፤ሕዝ2፥4፤ዘካ7፥11
9፥10 ዘፍ11፥3፤ 1ነገ7፥2-3፤አሞ7፥14፤ ሉቃ19፥4
9፥11 ኢሳ7፥8
9፥12 2ነገ16፥6፤2ዜና28፥18፤ኢዮ40፥11፤ መዝ79፥7፤ኢሳ5፥25

[*]2 ወይም፣ *በጨለማ ምድር*።
[°]6 ወይም፣ *ድንቅ፣ መካር*።

ይሁን እንጂ እግዚአብሔርን ወይም ገዢን የሚራገም ማንኛውም ሰው ጽኑ ቅጣት ይጠብቀዋል (ዘፀ 22፥28፤ ዘሌ 24፥15-16)።

9፥1 *የንፍታሌም፤* በ734 ና በ732 ዓ.ቅ.ክ የአሦሩ ቴልጌልቴልፌልሶር ሠላሳዊ እስራኤልን በወረረ ጊዜ፣ ይህ ነገድ ክፉኛ ተጐድቶ ነበር (2ነገ 15፥29)። *ገሊላ ያከብራል፤* "የባሕሩ መንገድ" (ማቴ 4፥13-15) በተባለው ከግብፅ ወደ ደማስቆ በሚወስደው አውራ መንገድ አጠገብ፣ በቅፍርናሆም ጌታ ኢየሱስ ወንጌልን በሰበከ ጊዜ ይህ ትንቢት ተፈጽሞአል (ማቴ 4፥13-15)።

9፥2 *ታላቅ ብርሃን፤* ኢየሱስና በእርሱ አማካይነት የሚገኘው ድነት ለአሕዛብ ብርሃን ነው (42፥6፤49፥6)።

9፥4 *ምድያም ድል በተመታ፤* ጌዴዎን ምድያማውያንን መታ፤ በእስራኤላውያን ላይ የጫኑትንም ቀንበር ሰበረ (መሳ 7፥22-25)። *የከበዳቸውን ቀንበር፤* በ10፥26-27 እግዚአብሔር የአሦራውያንን የጭቈና ቀንበር እንደሚሰብር ኢሳይያስ ተናግሮአል፤ ይህም ዓ.ቅ.ክ በ701 ላይ ተፈጽሞአል (37፥36-38 ይመ)።

9፥5 *ጫማ ... ልብስም፤* ከእንግዲህ ወዲያ ወታደራዊ ትጥቅ እንደማያስፈልግ ያመለክታል፤ የ2፥2-4 ማብ ይመ።

9፥6 *ወንድ ልጅ፤* ከመንግሥት ዘር የሆነ፣ የዳዊት ልጅ ነው (ቍ 7፤ 2ሳሙ 7፥14፤ መዝ 2፥7፤ ማቴ 1፥1፤ 3፥17፤ ሉቃ 1፥32 ይመ)። *ድንቅ መካር፤* አራቱ የመሲሑ የዙፋን ስሞች እያንዳንዳቸው ሁለት ክፍል አላቸው። አማኑኤል እንደሚባለው ስም (7፥14 ማብ ይመ)፣ እነዚህ የማዕረግ ስሞች እንደ ሌሎች የብሉይ ኪዳን ስሞች ሁሉ የተለመዱ ተራ ስሞች አይደሉም። "መካር" የሚለው ስም መሲሑ ንጉሥ እንደ ሆነ ሲያሳይ (ሚክ 4፥9)፣ በዕቅድ የሚሠራ መሆኑንም ያመለክታል (14፥27፤ መዝ 20፥4 ይመ)። እንደ ድንቅ መካር የሚመጣው የዳዊት ልጅ የሚያወጣው ዕቅድ ዓለምን ሁሉ የሚያስደንቅ ይሆናል። ይህ ዕቅድ በመጠኑ በምዕራፍ 11፣ በስፋት ከምዕራፍ 24-27 ተጠቅሶአል (25፥1 ይመ)። *ኀያል አምላክ፤* 10፥21 ይመ። እዚህ ላይ መለኮታዊ ኀይሉ ብርቱ ተዋጊ ሆኖ በአጽንዖት ተገልጦአል። *የዘላለም አባት፤* ዘላለማዊ፣ የሚራራና የሚሰጥ፣ የሚጠብቅም አምላክ መሆኑን የሚያሳይ ነው (ከ40፥9-11 ያነጻጽሩ)። *የሰላም ልዑል፤* አገዛዙ ምልአትንና ድነትን ለግለሰቦችና ለኅብረተ ሰቡ ያመጣል (11፥6-9 ይመ)።

9፥7 *እስከ ዘላለም...በጽድቅ ... በዳዊት ዙፋን፤* አካዝን የመሳሰሉ ነገሥታት የሠሩት ኀጢአት ቢኖርም እንኳ፣ ለዘላለም በጽድቅ የሚገዛው ክርስቶስ የሚመጣው ከዳዊት ቤት ነው (11፥3-5፤ 2ሳሙ 7፥12-13፡ 16፤ ኤር 33፥15፡20-22 ይመ)። *ቅናት ይህን፤* እግዚአብሔር እንደ ቀናተኛ አፍቃሪ ስለ ሆነ፣ ሕዝቡን አይተውም።

9፥9 *ኤፍሬምና፤* የ7፥2 ማብ ይመ።

9፥10 *ጡቦቹ ወድቀዋል፤* ከሸክላ ዐፈር ተሠርተው በፀሐይ የደረቁ ጡቦች በቀላሉ ይሰበራሉ። *በጥርብ ድንጋይ፤* አሞጽ በክፉዎች የተጠረቡትን ድንጋዮች ያወግዛል (አሞ 5፥11)። *በዝግባ፤* ጥንት በመካከለኛው ምሥራቅ የሊባኖስ ዝግባዎች እጅግ ተፈላጊዎች ነበሩ (1ነገ 7፥2-3)።

9፥11 *የረአሶንን ጠላቶች፤* አሦራውያንን ያመለክታል (የ7፥1 ማብ ይመ)።

9፥12፡17፡21 *ይህም ሁሉ ሆኖ ... አልበረደም፤* 5፥25 ይመ። ይህ አባባል በ10፥4 ላይም ተደግሞአል፤ በዚያ ሥፍራ ግን እግዚአብሔር በሕዝቡ መማረክ ቍጣው ገና አለመብረዱን ያሳያል።

[13]ሕዝቡ ግን ወደ ቀጣቸው ፊታቸውን አልመለሱም፤
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔርንም አልፈለጉም።
[14]ስለዚህ እግዚአብሔር ራስንና ጅራትን፣
የዘንባባውን ቅርንጫፍና ሸምበቆውን ከእስራኤል በአንድ ቀን ይቈርጣል።
[15]ሽማግሌዎችና የተከበሩ ሰዎች ራስ፣
ሐሰትን የሚያስተምሩ ነቢያት ደግሞ ጅራት ናቸው።
[16]ይህን ሕዝብ የሚመሩት ያስቱታል፤
የሚመራውም ሕዝብ ከመንገድ ወጥቶ ይባዝናል።
[17]ስለዚህ ጌታ በጐበዛዝት ደስ አይሰኝም፤
አባት ለሌላቸውና ለመበለቶች አይራራም፤
ሁሉም ፈሪሀ እግዚአብሔር ያላደረበትና ክፉ አድራጊ ነው፤
የሁሉ አፍ አስጸያፊ ቃል ይናገራልና።

ይህም ሁሉ ሆኖ፣ ቍጣው ገና አልበረደም፤
እጁም እንደተዘረጋ ነው።

[18]እንግዲህ ርኵሰት እንደ እሳት ይቀጣጠላል፤
እሾህንና ኵርንችትን ይበላል፤
ጥቅጥቅ ያለውን ደን ያነዳል፤
ጢሱም ተትጐልጕሎ እንደ ዐምድ ይቆማል።
[19]በሰራዊት ጌታ በእግዚአብሔር ቍጣ ምድር ትጋያለች፤
ሕዝቡም እሳት ውስጥ እንደሚጨመር ማገዶ ይሆናል፤
ወንድሙንም ማዳን የሚችል ማንም የለም።
[20]በቀኝ በኩል ይጐርሳሉ፤
ነገር ግን ራባቸው አይታገሥም፤
በግራም በኩል ይበላሉ፤
ነገር ግን አይጠግቡም፤
እያንዳንዱም የገዛ ወገኑን[a] ሥጋ ይበላል።
[21]ምናሴ ኤፍሬምን፣ ኤፍሬም ምናሴን ይበላል፤
በይሁዳም ላይ በአንድነት ይነሣሉ፤

ይህም ሁሉ ሆኖ፣ ቍጣው ገና አልበረደም፤
እጁም እንደ ተዘረጋ ነው።

10 ፍትሕ የጐደለውን ሕግ ለሚያወጡ፣
ጭቈና የሞላበትን ሥርዐት ለሚደነግጉ ወዮላቸው!
[2]የድኾችን መብት ለሚገፉ፣
የተጨቈነውን ሕዝቤን ፍትሕ ለሚያዛቡ፣
መበለቶችን ለሚበዘብዙ፣
ወላጅ የሌላቸውን ልጆች ለሚመዘብሩ ወዮላቸው!
[3]በምትጐበኙበት ቀን ምን ይውጣችኋል?
ጥፋት ከሩቅ ሲመጣስ ምን ትሆናላችሁ?
ርዳታን ለማግኘትስ ወደ ማን ትሸሻላችሁ?
ሀብታችሁንስ የት ታገኙታላችሁ?
[4]ከእስረኞች ጋር ከመርበትበት፣
ከታረዱትም ጋር ከመጣል በቀር ምንም አይተርፋችሁም።

ይህም ሁሉ ሆኖ፣ ቍጣው ገና አልበረደም።
እጁም እንደ ተዘረጋ ነው።

### የእግዚአብሔር ፍርድ በአሦር ላይ

[5]"የቍጣዬ በትር ለሆነ፣
የመቅሠፍቴም ዱላ በእጁ ላለው ለአሦራዊው ወዮለት!
[6]ሀብታቸውን እንዲዘርፍ፣ ምርኮን እንዲያግበሰብስ፣
እንደ መንገድ ላይ ጭቃም እንዲረግጣቸው፣
አምላክ በሌለው ሕዝብ ላይ እልከዋለሁ፣
በሚያስቈጣኝም ሕዝብ ላይ እሰደዋለሁ።
[7]እርሱ ግን እንዲህ አላሰበም፤
በልቡም ይህ አልነበረም፤
ነገር ግን ዕቅዱ ለማጥፋት፣
ብዙ ሕዝቦችንም ለመደምሰስ ነበር።
[8]እንዲህም ይል ነበር፤
'የጦር አዛዦቼ በሙሉ ነገሥታት አይደሉምን?
[9]ካልኖ እንደ ከርከሚሽ፣
ሐማት እንደ አርፋድ፣
ሰማርያስ እንደ ደማስቆ አይደሉምን?

9፥13 2ዜና28፥22፤ ኢሳ2፥3፤17፥7፤31፥1፤ 55፥6፤ኤር5፥3፤50፥4፤ ሕዝ7፥9፤ዳን9፥13፤ ሆሴ3፥5፤7፥7፡10፤ አሞ4፥6፡10፤ ሶፎ1፥6፤3፥7፤ ሐጌ2፥17
9፥14 ቍ14፡15፤ ኢሳ19፥15፤ራእ18፥8
9፥15 ኢዮ13፥4፤ ኢሳ3፥2-3፡8፤5፥13፤ 28፥7፤44፥20፤ ሕዝ13፥2፡22፤ ማቴ24፥24
9፥16 ኢሳ3፥12፤ ማቴ15፥14፤23፥16፡24
9፥17 ኢዮ5፥4፤ ኢሳ1፥4፤3፥8፤5፥25፤ 10፥6፤27፥11፤32፥6፤ ኤር9፥21፤11፥22፤ 13፥14፤18፥21፤ 48፥15፤49፥26፤ አሞ4፥10፤8፥13፤ ሚክ7፥2፤ማቴ12፥34፤ ሮሜ3፥13-14
9፥18 ዘዳ29፥23፤ መዝ83፥14፤ ኢሳ1፥31፤5፥6
9፥19 ኢዮ40፥11፤ መዝ97፥3፤ኢሳ1፥31፤ 3፥5፤13፥9፡13፤ ኤር17፥27
9፥20 ዘሌ26፥26፤ ኢዮ18፥12፤ ኢሳ49፥26፤ዘካ11፥9
9፥21 መሳ7፥22፤ 12፥4፤2ዜና28፥6፤ ኢሳ5፥25
10፥1 መዝ58፥2፤ ኢሳ5፥8
10፥2 ዘዳ10፥18፤ ኢዮ6፥27፤ኢሳ1፥17፤ 3፥14፤5፥23
10፥3 ቍ25፤ ኢዮ31፥14፤መዝ59፥5፤ 108፥12፤ኢሳ1፥24፤ 13፥6፤14፥23፤20፥6፤ 24፥6፤26፥14፤30፥7፤ 31፥3፤47፥11፤ኤር5፥9፤ 9፥9፤50፥15፤ ሉቃ19፥44
10፥4 ኢሳ5፥25፤ 12፥1፤22፥2፤24፥22፤ 34፥3፤63፥10፤64፥5፤ 66፥16፤ኤር4፥8፤ 30፥24፤39፥6፤ ሰቆ1፥12፤ናሆ3፥3፤ ዘካ9፥11
10፥5 ቍ12፡15፡18፡24፤2ነገ19፥21፤ኢሳ7፥20፤9፥4፤13፥3፡5፡13፤ 14፥5፡25፤26፥20፤28፥1፤30፥30፡31፤ 31፥8፤34፥2፤37፥7፤41፥15፤ 45፥1፤54፥16፤63፥6፤66፥14፤ ኤር50፥23፤ 51፥20፤ሕዝ30፥24-25፤ ሶፎ2፥13 10፥6 መሳ6፥4፤ 2ሳሙ22፥43፤2ዜና28፥9፤መዝ7፥5፤ ኢሳ5፥5፡29፤8፥1፤9፥17፡19፤37፥26-27፤ዕን1፥12 10፥7 ዘፍ50፥20፤ ሐሥ4፥23-28 10፥8 2ነገ18፥24 10፥9 ዘፍ10፥10፤14፥15፤ ዘኍ34፥8፤ 2ነገ16፥9፤17፥6፤18፥34፤2ዜና8፥4፤35፥20፤ኢሳ11፥11፤ ኤር49፥24

[a]20 ወይም፣ *ክንዱን*

9፥14 *ራስንና ጅራትን፣ የዘንባባውን ቅርንጫፍና ሸምበቆውን፤* የእስራኤልን መሪዎች ለማመልከት ነው (3፥1-3 ይመ)። ይህ አባባል የግብፅን መሪዎች በማመልከትም በ19፥15 ጥቅም ላይ ውሎአል።

9፥17 *አባት ለሌላቸውና ለመበለቶች፤* ብዙውን ጊዜ በኀይለኞች የሚጠቃ እነዚህ ናቸው፤ አሁን ግን እነርሱም ክፉዎች ሆነዋል (የ1፥17 ማብ ይመ)።

9፥18 *እሾኽንና ኵርንችትን፤* የ5፥6 ማብ ይመ።

9፥19 *እሳት ውስጥ እንደሚጨመር ማገዶ፤* ከቍ 5 ጋር ያነጻጽሩ።

9፥21 *ምናሴ ... ኤፍሬም፤* እነዚህ የሰሜኑ መንግሥት ሁለት ዋና ዋና ነገዶች ከሁለቱ የዮሴፍ ልጆች የተገኙ ናቸው (ዘፍ 46፥20፤ ዘፍ 48፥5-6 እና ማብ ይመ)። ከዘመናት በፊት እርስ በርሳቸው ይዋጉ ነበር (መሳ 12፥4)።

10፥1 *ወዮላቸው፤* በ5፥8-23ላይ ከተዘረዘሩት ወዮታዎች ጋር ያነጻጽሩ።

10፥2 *መበለቶችን ... ወላጅ የሌላቸውን ልጆች፤* የ1፥17፤ 9፥17 ማብ ይመ።

10፥4 *ከእስረኞች ... ከታረዱትም፤* 586 ዓ.ቅ.ክ ላይ ናቡከደነፆር ኢየሩሳሌምን በያዘ ጊዜ፣ የይሁዳ መሪዎች እንደ ሸሹ በኤር 39፥6-7 ላይ ተጠቅሶአል። *ይህም ሁሉ ሆኖ ... አልበረደም፤* የ9፥12፡17፡21 ማብ ይመ።

10፥5 *በትር ... ዱላ፤* 9፥4 እና ማብ ይመ፤ እግዚአብሔር ሌሎችን መንግሥታት ለመቅጣት፣ ባቢሎንን መዶሻ ወይም ዱላ አድርጎ ተጠቅሞባታል (ኤር 50፥23፤ 51፥20፤ ዕን 1፥6 ይመ)።

10፥6 *እንዲዘርፍ ... እንዲያግበሰብስ፤* በማኸር ሻላል ሃሽ ባዝ ትእምርት ፍጻሜ የመጨረሻ ክፍል ነው 8፥1-4 እና የ8፥3 ማብ ይመ። *አምላክ በሌለው ሕዝብ፤* ይሁዳን የሚመለከት ነው (ቍ 10 ይመ)።

10፥9 *ካልኖ፤* በሰሜን ሶርያ ያለ ግዛት ነው፤ በአሞጽ 6፥2 "ካልኔ" ተብላ የተጠራችውን ይመ። *ከርከሚሽ፤* ከካልኖ በስተ ምሥራቅ በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ የነበረ ትልቅ ምሽግ ነው (ኤር 46፥2 ይመ)። *ሐማት፤* በሰሎሞን ዘመን በሰሜን በኩል የእስራኤል መንግሥት ወሰን የነበረና በኦሮንቴስ ወንዝ ዳር የተመሠረተ ከተማ ነው (2ዜና 8፥4)፤ የ2ነገ 17፥24 ማብ ይመ። *አርፋድ፤* ከሐማት አጠገብ፣ ከካልኖ በስተ ደቡብ የነበረ ከተማ

[10]የጣዖታትን መንግሥታት፣
ምስሎቻቸው ከኢየሩሳሌምና ከሰማርያ
መንግሥታት የሚበልጡትን
እጄ እንደ ያዘች ሁሉ፣
[11]በሰማርያና በጣዖቶቿ ያደረግሁትን፣
በኢየሩሳሌምና በተቀረጹ ምስሎቿስ እንዲሁ
አላደርግምን?::”

[12]ጌታ በጽዮን ተራራና በኢየሩሳሌም ላይ የሚያደርገውን ሁሉ ከፈጸመ በኋላ፣ እንዲህ ይላል የአሦርን ንጉሥ ስለ ልቡ ትዕቢትና ስለ ንቀት አመለካከቱ እቀጣዋለሁ፤ [13]የአሦር ንጉሥ እንዲህ ይላልና፤

“‘ይህን ሁሉ ያደረግሁት በክንዴ ብርታት ነው፤
ደግሞም በጥበቤ አስተዋይ ነኝና::
የመንግሥታትን ድንበር አፈረስሁ፤
ሀብታቸውን ዘረፍሁ፤
ነገሥታታቸውን እንደ አንድ ኀያል ሆኜ
አዋረድሁ::[ᵀ]
[14]ሰው እጁን ወደ ወፍ ጎጆ እንደሚሰድ፣
እኔም እንዲሁ እጄን ወደ መንግሥታት
ሀብት ሰደድሁ፤
ሰዎች የተተወ ዕንቍላል እንደሚሰበስቡ፣
እኔም እንዲሁ ምድርን ሁሉ ሰበሰብሁ፤
ክንፉን ያራገበ የለም፤
አፉንም ከፍቶ የጮኸ አልነበረም::’ ”

[15]መጥረቢያ በሚቈርጥበት ሰው ላይ ይኵራራልን?
መጋዝስ በሚስበው ላይ ይታበያልን?
በትር በሚያነሣው ሰው ላይ ራሱን እንደሚ
ነቀንቅ፣
ዘንግም ራሱን ዕንጨት እንዳልሆነ አድርጎ
እንደሚኵራራ ነው::
[16]ስለዚህ ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
በፈረጠሙ ጦረኞቹ ላይ የሚያከሳ በሽታ
ይልካል፤
ከክብሩም በታች
እንደ ነበልባል የሚንቦገቦግ እሳት ይለኩሳል::
[17]የእስራኤል ብርሃን እሳት፣
ቅዱሱም ነበልባል ይሆናል፤
በአንድ ቀንም
እሾኹንና ኵርንችቱን እሳት ይበላዋል፤
[18]ሕመምተኛ እየመነመነ እንደሚሞት፣
የደኑን ክብርና የለማውን ዕርሻ፣
ነፍስና ሥጋንም ፈጽሞ ያጠፋል::
[19]በደኑ ውስጥ የሚተርፉት ዛፎች በጣም
ጥቂት ናቸው፤
ሕፃን ልጅ እንኳ ቈጥሮ ሊመዘግባቸው
ይችላል::

## የተረፉት የእስራኤል ዘሮች

[20]በዚያን ቀን ከእስራኤል ዘር የተረፉት፣
ከያዕቆብም ቤት የዳኑት፣
ከእንግዲህ ወዲህ
በመታቸው ላይ አይታመኑም፤
ነገር ግን በእስራኤል ቅዱስ *በእግዚአብሔር*
ላይ፣
በእውነት ይታመናሉ::
[21]የተረፉት ይመለሳሉ፣[ᵖ]
ከያዕቆብ ቤት የተረፉት ወደ ኀያሉ
አምላክ ይመለሳሉ::
[22]እስራኤል ሆይ፤

ሕዝብህ እንደ ባሕር አሸዋ ቢሆንም፣
የተረፉት ብቻ ይመለሳሉ::
ታላቅና ጻድቅ የሆነ ጥፋት ታውጇአል::
[23]ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
የወሰነውን ጥፋት በምድር ሁሉ ላይ ያመጣል::

[24]ስለዚህ ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
እንዲህ ይላል፤
“በጽዮን የምትኖሩ ሕዝቤ ሆይ፤
ግብፅ እንዳደረገብህ ሁሉ በትር ያነሡብህን፣
በሽመል የደበደቡህን

10፥10 2ነገ19፥18
10፥11 2ነገ19፥13፤ ኢሳ2፥8፤36፥18-20፤ 37፥10-13
10፥12 ቍ5፤ 2ነገ19፥7:31፤ መዝ18፥27፤ ኢሳ2፥11፤28፥21-22፤ 30፥31-33፤37፥36-38፤ 65፥7፤66፥4፤ ኤር5፥29፤50፥18፤ ሕዝ28፥17
10፥13 ዘዳ8፥17፤ 32፥26-27፤ ኢሳ14፥13-14፤47፥7፤ ሕዝ28፥4፤ዳን4፥30
10፥14 2ነገ19፥22-24፤ ኢዮ31፥25፤ ኢሳ14፥6፤37፥24-25፤ ኤር49፥16፤አብ1፥4፤ ዕን2፥6-11
10፥15 ቍ5፤ ኢሳ7፥20፤45፥9፤ ሮሜ9፥20-21
10፥16 ቍ18፤ ዘኍ11፥33፤ መዝ78፥31፤ኢሳ8፥7፤ 17፥4፤ኤር21፥14
10፥17 ዘኍ11፥1-3፤ 2ሳሙ23፥6፤ ኢዮ41፥21፤ኢሳ1፥31፤ 9፥18፤31፥9፤37፥23፤ ዘካ2፥5
10፥18 ቍ5፤ 2ነገ19፥23
10፥19 ቍ33-34፤ ኢሳ17፥6፤21፥17፤ 27፥13፤32፥19፤ ኤር44፥28
10፥20 ቍ27፤ 2ነገ16፥7፤ 2ዜና14፥11፤28፥20፤ ኢሳ1፥9፤5፥24፤ 11፥10:11፤12፥1:4፤ 17፥7፤19፥18:19፤ 24፥21፤28፥5፤48፥2፤ 50፥10፤52፥6፤ ኤር21፥2፤ሕዝ7፥16፤ ሆሴ3፥5፤6፥1፤ ሚክ3፥11፤7፥7፤ ዘካ9፥16
10፥21 ዘዳ45፥7፤ ኢሳ6፥13፤7፥3፤9፥6፤ ሶፎ3፥13

10፥22 ቍ23፤ ዘፍ12፥2፤ዕዝ1፥4፤ኢሳ11፥11፤28፥22፤46፥3፤ 48፥19፤ ኤር33፥22፤40፥2፤ዳን9፥27 10፥23 ቍ22፤ኢሳ6፥12፤ 28፥22፤ሮሜ9፥27-28 10፥24 ቍ5፤ዘፀ5፥14፤መዝ87፥5-6፤ኢሳ7፥4

[ᵀ]13 ወይም፣ *ኀይላቸውን አዋረድሁ*::
[ᵖ]21 በዚህና በቍ22 ላይ ዕብራይስጡ፣ *ሼር - ያሹብ* ይላል::

ነው:: እነዚህ ሁሉ ግዛቶች በ717 ዓ.ቅ.ክ ለአሦር መንግሥት ገብረዋል (36፥19 ይመ)::

10፥10 *ምስሎቻቸው ከኢየሩሳሌምና ከሰማርያ፤* እስራ ኤላዊ የሆነ ሁሉ ጣዖታትንና ምስሎቻቸውን እንዲያመልክ አይፈቀድለትም፤ ይሁን እንጂ ምድሪቱ በባዕድ አምልኮ ተሞልታ ነበር (2፥8):: ሰማርያ ከ722-721 ዓ.ቅ.ክ በሰልምናሶርና (2ነገ 17፥3-6) በሳርጎን ዳግማዊ ቍጥጥር ሥር ሆነች::

10፥12 *ትዕቢት፡* በትዕቢተኞች ላይ ፍርድ እንደሚመጣ በ2፥11:17 ላይ ተነግሮአል::

10፥13-14 *ነኝና ... ሆኜ፤* የአሦር ንጉሥ በትዕቢት ተኵ ራርቶ ስለ ራሱ ዘጠኝ ጊዜ ይናገራል፤ ከ14፥13-14፤ ሕዝ 28፥2-5 ጋር ያነጻጽሩ::

10፥15 *መጥረቢያ ... መጋዝስ ... በትር ... ዘንግም፤* ቍ 5፤ 9፥4 እና ማብ ይመ::

10፥16 *ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 1፥24 እና ማብ ይመ:: *የሚያከሳ በሽታ፤* 701 ዓ.ቅ.ክ ላይ የእግዚአብሔር መልአክ የአሦርን ንጉሥ የሰናክሬምን አንድ መቶ ሰማንያ አምስት ሺህ ወታደሮች የገደላቸው በፍጥነት በሚሠራጭ መቅሠፍት ሳይሆን አልቀረም (የ37፥36 ማብ፤ 2ሳሙ 24፥15-16፤ 1ዜና 21፥22:27 ይመ)::

10፥17:20 *ቅዱስ፤* የ1፥4 ማብ ይመ::

10፥18-19 *በደኑ ውስጥ ... ዛፎች፤* የአሦራውያንን ሰራ ዊት የሚያመለክት ነው፤ ቍ 33-34 ይመ::

*10፥19፤* ይህ የተፈጸመው በ612 ዓ.ቅ.ክ (በነነዌ መውደቅ) እንዲሁም በ605 ዓመት (በከርከሚሽ ጦርነት) መካከል ባለው ጊዜ ውስጥ ሳይሆን አይቀርም::

10፥20:27 *በዚያን ቀን፤* ተለይታ የምትታወቅ፣ ድልና ደስታ የሚገኝባት፣ “የእግዚአብሔር ቀን” ናት (የ2፥11:17:20፤ 9፥4 ማብ ይመ):: የእስራኤል መንግሥት ተመልሳ ትቆማለች፤ ሕዝቡም እግዚአብሔርን ያመሰግናሉ:: ይህን፣ “ቀን” ምዕራፍ 11 ከመሲሑ ዘመን ጋር ያያይዘዋል (11፥10-11፤ 12፥1-4 ይመ)::

10፥20-22 *የተረፉት፤* የ1፥9 ማብ ይመ:: በታማኝነት ጸንተው የተገኙት ትሩፋን በንጉሥ ሕዝቅያስ መሪነት 701 ዓ.ቅ.ክ ከነበረው ከአሦር ወረራ አምልጠዋል (37፥4 ይመ):: በኋላም ቀርተው የነበሩ እንደዚሁ ከባቢሎን ምርኮ ተመለሱ::

10፥20 *በመታቸው ላይ፤* የአሦርን ንጉሥ የሚያመለክት ነው (የ7፥17 ማብ ይመ)::

10፥21 *ኀያሉ አምላክ፤* የ9፥6 ማብ ይመ::

10፥22 *እንደ ባሕር አሸዋ፤* የዘፍ 13፥16፤22፥17 ማብ ይመ:: *ጥፋት ታውጇአል፤* እስራኤል ኀጢአት ስለ ሠራ፣ እግዚ አብሔር ሕዝቡን በውጭ ወራሪዎች ይቀጣቸዋል::

10፥23-24 *ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 1፥24 እና ማብ ይመ::

10፥24 *በትር ... ሽመል፤* ቍ 5፤ 9፥4 እና ማብ ይመ::

አሦራውያንን አትፍራቸው::
[25]በአንተ ላይ ያመጣሁትን ቅጣት በጥቂት
ጊዜ ውስጥ አቆማለሁ፤
በእነርሱም ላይ መቅሠፍቴን አመጣለሁ::"

[26]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ምድያምን
በሔሬብ ዐለት አካባቢ እንደ መታ፣
በጅራፍ ይገርፋቸዋል፤
በግብፅ እንዳደረገውም ሁሉ፣
በትሩን በውሆች ላይ ያነሣል::
[27]በዚያን ቀን ሸክማቸው ከትከሻህ፣
ቀንበራቸውም ከዐንገትህ ላይ ይነሣል፤
ከውፍረትህም የተነሣ
ቀንበሩ ይሰበራል::[a]

[28]ወደ ዐያት ይገባሉ፣
በሚግሮን ያልፋሉ፤
ጓዛቸውንም በማክማስ ያከማቻሉ::
[29]መተላለፊያውን ዐልፈው እንዲህ ይላሉ፤
"በጌባዕ ሰፍረን እናድራለን::"
ራማ ደነገጠች፤
የሳኦል ከተማ ጊብዓ ሸሸች::
[30]የጋሊም ሴት ልጅ ሆይ፤ ጩኺ!
ላይሻ ሆይ፤ አድምጪ!
ምስኪን ዓናቶት ሆይ፤ መልሺላት!
[31]ማድሜናህ በሽሽት ላይ ነች፤
የጌቢም ሕዝብ ሊደበቅ ይሮጣል::
[32]በዚህ ቀን ኖብ ይደርሳሉ፤
እጃቸውን በኢየሩሳሌም ኰረብታ፣
በጽዮን ሴት ልጅ ተራራ ላይ በዛቻ ነቀነቁ::
[33]እነሆ፤ ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
በታላቅ ኀይል ቅርንጫፎችን ይቈራርጣል፤
ረጃጅም ዛፎች ይገነደሳሉ፤
ከፍ ከፍ ያሉትም ይወድቃሉ::
[34]ጥቅጥቅ ያለውን ደን በመጥረቢያ ይቈራርጣል፤
ሊባኖስም በኀያሉ ፊት ይወድቃል::

10፥25 ቍ3:5፤ መዝ30፥5፤ኢሳ13፥5፤ 17፥14፤24፥21፤ 26፥20፤29፥17፤ 30፥30፤34፥2፤66፥14፤ ዳን8፥19፤11፥36፤ ሚክ5፥6፤ሐጌ2፥6
10፥26 ዘፀ14፥16፤ ኢሳ9፥4፤30፥32፤ 37፥36-38
10፥27 ቍ20፤ ዘሌ26፥13፤ መዝ66፥11፤ኢሳ9፥4፤ 14፥25፤47፥6፤52፥2፤ ኤር30፥8
10፥28 ኢያ1፥11፤ 1ሳሙ13፥2፤14፥2
10፥29 ኢያ18፥24: 25፤መሳ19፥14፤ ነህ11፥31፤ኢሳ15፥5
10፥30 1ሳሙ25፥44፤ ነህ11፥32
10፥32 1ሳሙ21፥1፤ ኢዮ15፥25፤መዝ9፥14፤ ኢሳ16፥1፤ኤር6፥23
10፥33 ዘፀ12፥12፤ ኢሳ2፥13፤5፥15፤ 18፥5፤27፥11፤ ሕዝ17፥4፤አሞ2፥9
10፥34 ዘፍ49፥24፤ 2ነገ19፥23፤ መዝ93፥4፤ኢሳ33፥21፤ ናሆ1፥12፤ዘካ11፥2
11፥1 ቍ10፤ 2ነገ19፥26:30፤ ኢዮ14፥7፥8፤ ኢሳ4፥2፤9፥7፤27፥6፤ ማቴ1፥1፤ራእ4፥2፤ 9፥7፤27፥6፤ማቴ1፥1፤ ራእ5፥5
11፥2 ዘፀ28፥3፤ መሳ3፥10፤ኢሳ9፥6፤ 32፥15፤42፥1፤44፥3፤ 48፥16፤59፥21፤61፥1፤ ሕዝ37፥14፤39፥29፤ ኢዩ2፥28፤ማቴ3፥16፤ ዮሐ1፥32-33፤16፥13፤ ኤፌ1፥17፤ቈላ2፥3፤ 2ጢሞ1፥7
11፥3 ኢሳ33፥6፤

## ከእሴይ ግንድ የወጣ ቍጥቋጥ

**11** ከእሴይ ግንድ ቍጥቋጥ ይወጣል፤
ከሥሮቹም አንዱ ቅርንጫፍ ፍሬ
ያፈራል::
[2]የእግዚአብሔር መንፈስ፣
የጥበብና የማስተዋል መንፈስ፣
የምክርና የኀይል መንፈስ፣
የዕውቀትና እግዚአብሔርን የመፍራት
መንፈስ ያርፍበታል::
[3]እግዚአብሔርን በመፍራት ደስ ይለዋል፤
ዐይኑ እንዳየ አይፈርድም፤
ጆሮውም እንደ ሰማ አይበይንም::
[4]ነገር ግን ለድኾች በጽድቅ ይፈርዳል፤
ለምድር ምስኪኖችም ፍትሕን ይበይናል፤
በአፉ በትር ምድርን ይመታል፤
በከንፈሩም እስትንፋስ ክፉዎችን ይገድላል::
[5]ጽድቅ የወገቡ መታጠቂያ፣
ታማኝነትም የጐኑ መቀነት ይሆናል::

[6]ተኵላ ከበግ ጠቦት ጋር ይኖራል፤
ነብርም ከፍየል ግልገል ጋር ይተኛል፤
ጥጃ፣ የአንበሳ ደቦልና የሰባ ከብት[b] በአንድነት
ይሰማራሉ፤
ትንሽ ልጅም ይመራቸዋል::
[7]ላምና ድብ በአንድነት ይሰማራሉ፤
ልጆቻቸውም አብረው ይተኛሉ፤
አንበሳም እንደ በሬ ገለባ ይበላል::
[8]ጡት የሚጠባ ሕፃን በእፉኝት ጕድጓድ
ላይ ይጫወታል፤

ዮሐ2፥25፤7፥24 11፥4 ኢዮ4፥9፤5፥16፤40፥18፤መዝ2፥9፤18፥8፤ 72፥2:4፤139፥19፤ኢሳ3፥14፤9፥7፤14፥30፤27፥7፤30፥28:31:33፤ 40፥24፤59፥19፤ሕዝ21፥31፤ዘካ14፥12፤ሚል4፥6፤2ተሰ2፥8፤ ራእ19፥11:15 11፥5 ዘፀ12፥11፤1ነገ18፥46፤ ኢሳ25፥1፤ኤፌ6፥14 11፥6 ኢሳ65፥25 11፥7 ኢዮ40፥15 11፥8 ኢሳ14፥29፤ 30፥6፤59፥5፤65፥20

[a]27 ዕብራይስጡ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ግን፣ *ቀንበሩ ከትከሻህ ላይ ይሰበራል* ይላል::
[b]6 ዕብራይስጡ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ግን፣ *የሰባ አንበሳ ይበላል* ይላል::

10፥26-27 *ምድያምን ... ሸክማቸው ... ቀንበራቸውም፤* የ9፥4 ማብ ይመ::

10፥26 *በሔሬብ፤* ከምድያም መሪዎች አንዱ ነው (መሳ 7፥25):: *በግብፅም ... በውሆች፤* ሙሴ በቀይ ባሕር ላይ እጁን በዘረጋ ጊዜ፣ ውሃው የፈርዖንን ሠረገሎች አሰጠማቸው (ዘፀ 14፥26-28 ይመ)::

10፥27 *ከውፍረትህም፤* እንደ ሰባ እንስሳ፣ እስራኤል ቀንበሩን መስበር ይችላል::

*10፥28-32፤* የአሦራውያን ሰራዊት ከከተማይቱ በስተ ሰሜን ዐሥራ ስድስት ኪሎ ሜትር ያህል ወደ ኢየሩሳሌም ስለ መጠጋቱ ኢሳይያስ ራእይ እንደሚያይ ሆኖ ይናገራል::

10፥28 *ማክማስ፤* ከኢየሩሳሌም በስተ ሰሜን ዐሥራ አንድ ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ ትገኛለች::

10፥29 *ራማ፤* የሳሙኤል አገር ናት:: ከኢየሩሳሌም 8 ኪሎ ሜትር ያህል ትርቃለች (1ሳሙ 7፥17):: *የሳኦል ከተማ ጊብዓ፤* ከኢየሩሳሌም 5 ኪሎ ሜትር ያህል ትርቃለች:: የመጀመሪያው የእስራኤል ንጉሥ ዋና ከተማ ነበረች (1ሳሙ 10፥26 ይመ)::

10፥30 *ምስኪን ዓናቶት፤* የኤርምያስ ከተማ ናት (ኤር 1፥1 ይመ)::

10፥32 *ኖብ፤* በኢየሩሳሌም አጠገብ ያለው የእስኮፐዮስ ተራራ ሊሆን ይችላል:: *በጽዮን ሴት ልጅ፤* ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን የሚገልጥ ዘይቤያዊ አባባል ነው::

10፥33 *ጌታ፣ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 1፥24 እና ማብ ይመ:: *ቅርንጫፎችን ... ዛፎች፤* ሰናክሬምና ሰራዊቱ ይወድቃሉ (ቍ 16-19 እና ማብ ይመ)::

10፥34 *ሊባኖስም፤* የታወቀ የሊባኖስ ዝግባዎችን ያመለክታል (2፥13 እና ማብ ይመ)::

11፥1 *እሴይ፤* የዳዊት አባት ነው (1ሳሙ 16፥10-13 ይመ):: *ግንድ ቍጥቋጥ፤* አሦራውያን ከይሁዳ በቀር ሁሉን አጥፍተዋል፤ የይሁዳን መንግሥት እንዲያበቃ ያደረገው ግን በ586 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎናውያን ያካሄዱት ወረራና ምርኮ ነው:: መሲሑ ከዳዊት የዘር ግንድ እንደ ቍጥቋጥ ያድጋል 6፥13 እና ማብ ይመ:: *ቅርንጫፍ፤* የ4፥2፤ ማቴ 2፥23 ማብ ይመ::

11፥2 *የእግዚአብሔር መንፈስ ... ያርፍበታል፤* ልክ እንደ ዳዊት ሁሉ መሲሑ (1ሳሙ 16፥13) የመንፈስ ቅዱስን ኀይል ይለብሳል ማለት ነው:: *የምክርና የኀይል፤* ለማድረግ ያሰበውንና የወጠነውን በትክክል እንዲያቅድ ያቀደውንም ዳር እንዲያደርስ መንፈስ ቅዱስ ብርታትንና ኀይልን ያድለዋል (የ9፥6 ማብ ይመ):: *እግዚአብሔርን የመፍራት፤* ምሳ 1፥7 ይመ::

11፥3 *እግዚአብሔርን በመፍራት ደስ ይለዋል፤* ዮሐ 8፥29 ይመ::

11፥4 *በጽድቅ ... ፍትሕን፤* በኢሳይያስ ዘመን የነበሩ ገዦች ጽድቅና ፍትሕ አያደርጉም ነበር (1፥17፤ 5፥7፤ የ9፥7 ማብ ይመ):: *በአፉ በትር፤* በ10፥5:24 እንደ ተገለጸው አሦር የእግዚአብሔር በትር ነው፤ መሲሑ ግን አሕዛብን በብረት በትር ይገዛል (መዝ 2፥9፤ ራእ 19፥5)::

11፥5 *መታጠቂያ፤* አንድ ሰው ጕልበት የሚጠይቅ ሥራ ለመሥራት ቈርጦ ሲነሣ፣ የተንዘረፈፈውን ልብሱን ሰብስቦ አድርጎ በመቀነት ይታጠቀዋል፤ (5፥27 ይመ)::

*11፥6-9፤* በመሲሑ ዘመን የሚኖረው ሰላምና ጸጥታ፣ ሕፃናት አስፈሪ ከነበሩ አራዊት ጋር እንኳን ቢጫወቱ እንደማይጐዱ ያመለክታል:: እነዚህ ሁኔታዎች የሚመጣውን የመሲሑን መንግሥት

ጡት የባለም ሕፃን እጁን በእፉኝት
ጕድጓድ ይከትታል።
[9]በተቀደሰው ተራራዬ ሁሉ ላይ
ጕዳት ወይም ጥፋት አያደርሱም፤
ውሃ ባሕርን እንደሚሸፍን፣
ምድር ሁሉ እግዚአብሔርን በማወቅ
ትሞላለችና።

[10]በዚያን ቀን፣ የእሴይ ሥር ለሕዝቦች ምልክት ሆኖ ይቆማል፤ መንግሥታት ወደ እርሱ ይመጣሉ፤ ማረፊያውም የከበረ ይሆናል። [11]በዚያን ቀን፣[ነ] ጌታ እጁን ዘርግቶ እንደ ገና የተረፈውን የሕዝቡን ቅሬታ ከአሦር፣ ከታችኛው ግብፅ፣ ከላይኛው ግብፅ፣ ከኢትዮጵያ፣ ከኤላም፣ ከባቢሎን፣ ከሐማትና ከባሕር ጠረፍ ምድር ይሰበስባል።

[12]ለመንግሥታት ምልክትን ያቆማል፤
ከእስራኤልም የተሰደዱትን መልሶ ያመ
ጣቸዋል፤
የተበተኑትን የይሁዳ ሕዝብ፣
ከአራቱ የምድር ማእዘን ይሰበስባል።
[13]የኤፍሬም ምቀኝነት ያከትማል፤
የይሁዳ ጠላቶችም[ጣ] ይቈረጣሉ፤
ኤፍሬም በይሁዳ አይቀናም፤
ይሁዳም ኤፍሬምን አይጠላም።
[14]በምዕራብ በኩል በፍልስጥኤም ተረተር ላይ
ይወርዳሉ፤
ሁለቱም ተባብረው በምሥራቅ ያለውን
ሕዝብ ይዘርፋሉ፤
በኤዶምና በሞዓብ ላይ እጃቸውን ያነሣሉ፤
አሞናውያንም ይገዙላቸዋል።
[15]እግዚአብሔር
በሚጋረፍም ነፋስ
የግብፅን ባሕረ ሰላጤ ያደርቃል፤
እጁን በኤፍራጥስ ወንዝ[ጨ] ላይ ይዘረጋል፤
ሰባት ታናናሽ ጅረትም አድርጎ ይለያየዋል፤
ስለዚህ ሰዎች ከነጫማቸው መሻገር ይችላሉ።
[16]እስራኤል ከግብፅ በወጣ ጊዜ
እንደ ሆነው ሁሉ፣
ከአሦር ለተረፈው ቅሬታ ሕዝብ፣
እንዲሁ ጐዳና ይዘጋጅለታል።

## የውዳሴ መዝሙር

**12** በዚያን ቀን እንዲህ ትላለህ፤
"እግዚአብሔር ሆይ፤
ቀድሞ ተቈጥተኸኝ ነበር፤
አሁን ግን ከቍጣህ ተመለስህ፤
ደግሞም አጽናንተኸኛልና እወድስሃለሁ።
[2]እነሆ፣ እግዚአብሔር ድነቴ ነው፤
እታመናለሁ፣ ደግሞም አልፈራም፤
*ጌታ እግዚአብሔር ብርታቴና ዝማሬዬ ነው፤
ድነቴም ሆኖአል።"

11፥9 ዘፀ7፥5፤ ዘኍ25፥12፤ 1ሳሙ17፥46፤ መዝ48፥1፤98፥2-3፤ ኢሳ2፥2:4፤9፥7፤ 19፥21፤45፥6:14: 22፤48፥20፤49፥26፤ 52፥10፤ኤር24፥7፤ 31፥34፤ዕን2፥14
11፥10 ቍ1፤ መዝ20፥5፤116፥7፤ ኢሳ2፥4፤10፥20፤ 14፥1:3፤18፥3፤ 28፥12፤32፥17-18፤ 40፥2፤49፥23፤ 56፥3:6፤ 60፥5:10፤ኤር4፥6፤ 6፥16፤30፥10፤46፥27፤ ሐጌ2፥9፤ዘካ2፥5፤ ሉቃ2፥32፤ዮሐ12፥32፤ ሐሥ11፥18፤ ሮሜ15፥12
11፥11 ዘፍ10፥6:22፤ ዘዳ30፥4፤ኢሳ1፥9፤ 10፥9:20፤19፥24፤ 24፥15፤41፥1:5፤ 42፥4:10:12፤49፥1: 12፤51፥5፤59፥18፤ 60፥9፤66፥19፤ ኤር16፥15፤44፥1:15፤ 46፥27፤ሕዝ29፥14፤ 30፥14፤38፥8፤ ሆሴ11፥11፤ ሚክ7፥12፤ዘካ8፥7፤ 10፥10፤ሐሥ8፥27
11፥12 ነህ1፥9፤ መዝ20፥5፤48፥10፤ 67፥7፤106፥47፤ ኢሳ14፥1:2፤41፥5:14፤ 43፥5፤49፥5:22፤ 54፥7፤ኤር16፥15፤ 31፥10፤32፥37፤ ሕዝ28፥25፤ሶፎ3፥10፤ ራእ7፥1
11፥13 2ዜና28፥6፤ ኤር3፥18፤ሕዝ37፥16-17:22፤ሆሴ1፥11 11፥14 ዘኍ24፥18፤ መሳ6፥3፤ 11፥14-18፤2ዜና26፥6፤28፥18፤ መዝ137፥7፤ኢሳ15፥1፤ 16፥14፤ 25፥3:10፤34፥5-6፤60፥12፤ 63፥1፤ኤር48፥40፤49፥22፤ ሕዝ25፥12፤ዳን11፥41፤ኢዩ3፥19፤ አብ1፥1፤ሶፎ2፥8:11፤ሚል1፥4
11፥15 ዘፍ41፥6፤ዘፀ14፥22:29፤ ዘዳ11፥10፤ኢሳ7፥20፤ 19፥16፤30፥32፤37፥25፤42፥15፤ኤር50፥38፤ 51፥36
11፥16 ቍ11፤ ዘፍ45፥7፤ዘፀ14፥26-31፤ኢሳ19፥23፤35፥8፤40፥3፤ 49፥11፤51፥10፤ 57፥14፤62፥10፤ኤር50፥5 12፥1 ኢዮ13፥16፤ መዝ9፥1:71፥21፤ኢሳ10፥20፤25፥1 12፥2 ዘፀ15፥2፤ኢዮ13፥15፤ መዝ18፥1፤ 26፥1፤112፥7፤ኢሳ17፥10፤ 25፥9፤ 26፥3:4፤33፥6፤ 38፥11፤45፥17፤51፥5:6፤54፥8፤59፥16፤ 61፥10፤ 62፥11፤ዳን6፥23

[ነ]11 ዕብራይስጡ፣ *ከጳትሮስ* ይላል።
[ጣ]13 ወይም፣ *ባላንጣዎቹ*።
[ጨ]15 ዕብራይስጡ *ወንዙ* ይላል።
*እግዚአብሔር በሚለው ስም ፈንታ ተተክቶ የገባ ነው

ፍጹምነት የሚገልጡ ናቸው 2፥2-4 እና ማብ ይመ፤ 35፥9፤ 65፥20-25፤ ሕዝ 34፥25-29 ይመ።

11፥9 *በተቀደሰው ተራራዬ፤* 2፥2-4 እና ማብ ይመ። *በማወቅ ትሞላለችና፤* የጌታ ትምህርት በኢየሩሳሌም የተሰጠበትን 2፥3 ይመ።

11፥10 *በዚያን ቀን፤* የ10፥20፡27 ማብ ይመ። *የእሴይ ሥር፤* ከቍ 1 ጋር በጣም የሚቀራረብ የመሲሑ የማዕረግ ስም ነው (53፥2፤ ሮሜ 15፥12፤ ራእ 5፥5፤ 22፥16 ይመ)። *ምልክት፤* 5፥26 እና ማብ ይመ።

11፥11 *እንደ ገና፤* የመጀመሪያው ከግብፅ የወጡበት ጊዜ ነው (ቍ 16 ይመ)። ምናልባት ሁለተኛው ከአሦርና ከባቢሎን ምርኮ የተመለሱበትን የሚያመለክት ይሆናል። ይሁን እንጂ አንዳንድ ተርጓሚዎች ይህ ክፍል ኢየሩሳሌም በ70 ዓ.ም. ከተደመሰሰች በኋላ የነበረውን የሕዝቡን መበታተን እንደሚያመለክት የሚያምኑ፣ እንደገና መሰብሰቡ በክርስቶስ ዳግም ምጽአት የሚፈጸም እንደሆነ ያስባሉ። *የተረፈውን፤* የ1፥9፤10፥20-22 ማብ ይመ። *ከታችኛው ግብፅ፤* በሰሜን በኩል ያለው የወባይ መፋሰሻ (ወንዙ ወደ ሜዲቴራንያን ባሕር የሚገባበት) አውራጃ ነው። *ከላይኛው ግብፅ፤* ደቡባዊው የግብፅ ምድር። *ኤላም፤* ከታችኛው ጢግሮስ ሸለቆ በስተ ሰሜን ምሥራቅ ያለው ምድር ነው (21፥2፤ ኤር 49፥34-39፤ ዳን 8፥1 ይመ)። *ሐማት፤* የ10፥9 ማብ ይመ። *ከባሕር ጠረፍ ምድር፤* በሜዲትራኒያን ባሕር ጠረፍ ያሉትን ከተሞች የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (41፥1:5፤ 42፥4፤ ዘፍ 10፥5 ይመ)።

11፥12 *የተሰደዱትን መልሶ ያመጣቸዋል፤* 27፥13፤ 49፥22፤ 56፥8፤ 62፥10፤ 66፥20 ይመ። *ከአራቱ የምድር ማእዘን፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ከአራቱ ክንፎች" ማለት ሲሆን፣ አቻ ትርጕሙ ግን "ከምድር ዳርቻዎች" ማለት ነው (24፥16፤ ኢዮ 37፥3 ይመ)።

11፥13 *የኤፍሬም ምቀኝነት፤* የ7፥2 ማብ ይመ። ከምርኮ በፊት ኤፍሬምና ይሁዳ በየጊዜው እርስ በርሳቸው ይዋጉ ነበር (9፥21 ይመ)።

11፥14 *በምሥራቅ ያለውን ሕዝብ፤* ምናልባት እስራኤልን የዘረፉትን ምድያማውያንንና ሌሎቹን የምሥራቅ ሕዝቦች ይመለከታል (9፥4 ይመ)። *በኤዶምና በሞዓብ ... አሞናውያንም፤* ከግብፅ ከወጡ በኋላ እስራኤላውያን እነዚህን ሕዝቦች አልወጉም (መሳ 11፥14-18 ይመ)። እስራኤላውያን ወደ ፊት አካባቢውን ሁሉ እንደሚቈጣጠሩ በ14፥2፡ 49፥23፤ 60፥12 ተጠቅሶአል (25፥10፤ 34፥5 ይመ)።

11፥15 *የግብፅን ባሕረ ሰላጤ ያደርቃል፤* እስራኤል ከግብፅ በወጡ ጊዜ ቀይ ባሕር መድረቁን የሚጠቁም ነው (ዘፀ 14፥21-22 ይመ)። *በኤፍራጥስ፤* ራእ 16፥12 የኤፍራጥስን ወንዝ መድረቅ ያመለክታል፤ የነገሥታትን ግሥጋሴ የሚያግዱ ዕንቅፋቶችን መወገድ ለማመልከት በትእምርታዊ አገላለጽ የተነገረ ሳይሆን አይቀርም።

11፥16 *ጐዳና፤* ዕንቅፋት የሆኑት ነገሮች እንደሚወገዱና ወደ ኢየሩሳሌም የሚወስደው አውራ ጐዳናም እንደሚሠራ በ57፥14፤ 62፥10 ተገልጾአል (ከ40፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ)።

*12፥1-6፤* የእግዚአብሔርን ታዳጊነት ለመግለጥ የተዘመሩ ሁለት አጫጭር የምስጋና መዝሙሮች በነዚህ ቍጥሮች ውስጥ ተካተዋል (ቍ 1-3፡4-6 ይመ)፤ እነዚህ መዝሙሮች ከም 7-11 ላይ በከፍተኛ ደረጃ የተገለጸውን ዐቢይ ቁም ነገር የሚያመለክቱ ናቸው (የ7፥1-12፥6 ያለውን ማብ ይመ፤ የ6፥1 ማብ ይመ)።

12፥1:4 *በዚያን ቀን፤* የ10፥20:27 ማብ ይመ።

12፥1 *እወድስሃለሁ፤* ምናልባትም ሕዝቡ እግዚአብሔር ስለሚታደገው በእርግጠኝነት ያቀረበው ውዳሴ ነው። *ከቍጣህ ተመለስህ፤* የ9፥12:17:21 ማብ ይመ። እግዚአብሔር እስራኤልን ከቀጣ በኋላ፣ ቍጣው አሦርንና ባቢሎንን በመሳሰሉ አገሮች ላይ ይወርዳል።

12፥2፤ *ጌታ፣ እግዚአብሔር፤* የእግዚአብሔር የተጸውዖ ስሙ ለየት ባለ መንገድ መገለጹን ያመለክታል። የመጀመሪያው "ያህ" ማለት ሲሆን፣ ሁለተኛው ግን ምናልባት ያህዌ ተብሎ የሚነበብ ሳይሆን አይቀርም የዘፀ 3፥15 ማብ ይመ። *ድነቴም፤* ከዘፀ 15፥2 የተወሰደ ጥቅስ ሲሆን፣ ግብፃውያን በቀይ ባሕር ሰጥመው

3ከድነቴ ምንጮች
ውሃ በደስታ ትቀዳላችሁ::

4በዚያን ቀን እንዲህ ትላላችሁ፤
"*እግዚአብሔርን አመስግኑ፤ ስሙንም ጥሩ፤*

ያደረገውንም በአሕዛብ መካከል አስታውቁ፤
ስሙ ከፍ ከፍ ማለቱንም ዐውጁ::
5*ለእግዚአብሔር ዘምሩ፤ ታላቅ ሥራ ሠርቶአልና፤*
ይህም ለዓለም ሁሉ ይታወቅ::
6የጽዮን ሕዝብ ሆይ፤ እልል በሉ፤ በደስታም ዘምሩ፤
በመካከላችሁ ያለው የእስራኤል ቅዱስ ታላቅ ነውና::

## በባቢሎን ላይ የተነገረ ትንቢት

**13** የአሞጽ ልጅ ኢሳይያስ ስለ ባቢሎን ያየው ንግር፤

2ባተራቈተ ኰረብታ ዐናት ላይ ምልክት ስቀሉ፤
ድምፃችሁን ከፍ አድርጋችሁ ጩኹ፤
በመሳፍንቱም በር እንዲገቡ፣
በእጅ ምልክት ስጡ::
3በድል አድራጊነቴ ደስ የሚላቸውን
ቅዱሳኔን አዛለሁ፤
ቍጣዬንም እንዲፈጽሙ፣
ተዋጊዎቼን ጠርቻለሁ::

4በተራሮች ላይ እንደ ብዙ ሕዝብ ድምፅ፣
የሚሰማውን ጩኸት አድምጡ!
በመንግሥታትም መካከል፣
እንደ ተጨናንቀ ሕዝብ ድምፅ የሆነውን
ውካታ ስሙ!
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ሰራዊቱን ለጦርነት አሰልፎአል::
5*እግዚአብሔርና የቍጣው ጦር መሣሪያ፣*
ምድሪቱን በሙሉ ለማጥፋት፣
ከሩቅ አገር፣
ከሰማያትም ዳርቻ መጥተዋል::

6*የእግዚአብሔር ቀን ቀርቦአልና አልቅሱ፤*
ሁሉን ቻይ[a] ከሆነ አምላክ ዘንድ ጥፋት
ይመጣልና::
7ስለዚህ እጆች ሁሉ ሽባ ይሆናሉ፤
የሰውም ሁሉ ልብ ይቀልጣል::
8ሽብር ይይዛቸዋል፤
ሥቃይና ጭንቀት ይደርስባቸዋል፤
ምጥ እንደ ያዛት ሴት ያምጣሉ፤
እርስ በርሳቸው በድንጋጤ ይተያያሉ፤
ፊታቸውም በፍርሀት ቀይ ይሆናል::
9እነሆ፤ *የእግዚአብሔር ቀን ጨካኝ ነው፤*
ምድርን ባድማ ሊያደርጋት፣
በውስጧም ያሉትን ኀጢአተኞች ሊያጠፋ፣
ከመዓትና ከብርቱ ቍጣ ጋር ይመጣል::

12፥3 ዘፀ15፥2፤ 2ነገ3፥17፤መዝ36፥9፤ ኤር2፥13፤17፥13፤ ዮሐ4፥10፡14
12፥4 ዘፀ3፥15፤ መዝ80፥18፤105፥1፤ 113፥2፤ኢሳ10፥20፤ 24፥15፤25፥1፤26፥8፡ 13፤54፥5፤60፥3፤ ኤር10፥7፤ሶፎ2፥11፤ ሚል1፥11
12፥5 ዘፀ15፥1፤ መዝ98፥1
12፥6 ዘፍ21፥6፤ መዝ46፥5፤48፥1፤ 78፥41፤98፥4፤99፥2፤ ኢሳ1፥24፤10፥20፤ 17፥7፤24፥14፤29፥19፤ 37፥23፤43፥3፡14፤ 45፥11፤48፥20፤ 49፥26፤52፥8፤55፥5፤ ኤር20፥13፤31፥7፤ ሕዝ39፥7፤ሶፎ3፥14-17፤ ዘካ2፥10
13፥1 ቍ19፤ ዘፍ10፥10፤ኢሳ1፥1፤ 14፥4፡28፤15፥1፤ 20፥2፤21፥1፡9፤ 37፥2፤46፥1-2፤ 48፥14፤ኤር24፥1፤ 25፥12፤ናሆ1፥1፤ ዕን1፥1፤ዘካ9፥1፤12፥1፤ ሚል1፥1፤ራእ14፥8
13፥2 መዝ20፥5፤ ኢሳ24፥12፤45፥2፤ ኤር50፥2፤ 51፥27፡58
13፥3 ቍ17፤ ኢዮ40፥11፤መዝ149፥2፤ ኢሳ10፥5፤21፥2፤ ኤር51፥11፤ ጾን5፥28፡31፤ኢል3፥11 13፥4 መዝ46፥6፤ኢሳ42፥13፤46፥6፤ 47፥4፤51፡15፤ኤር50፥41፤ኢል3፥14 13፥5 ኢሱ6፥17፤ኢሳ5፥26፤ 10፥25፤24፥1፤30፥25፤34፥2፤45፥1፤ 54፥16፤ኤር50፥25
13፥6 ዘፍ17፥1፤ኢሳ2፥12፤10፥3፤14፥15፡31፤15፥2፤16፥7፤23፥1፤ ሕዝ30፥2፤ያዕ5፥1 13፥7 ኢሱ2፥11፤ 2ነገ19፥26፤ኢዮ4፥3፤ ኤር47፥3፤ሕዝ21፥7 13፥8 ዘፍ3፥16፤ዘፀ15፥14፤መዝ31፥13፤48፥5፤ ኢሳ21፥4፤ኢል2፥6፤ናሆ2፥10፤ዮሐ16፥21 13፥9 ኢሳ2፥12፤9፥19፤ 26፥21፤66፥16፤ኤር6፥23፤25፥31፤51፥2፤ኢል3፥2

[a]6 ዕብራይስጡ *ሻዳይ* ይላል::

የተሸነፉበትን ጊዜ ያስታውሳል (መዝ 118፥14 ይመ)::

12፥3 *ምንጮች፤* እስራኤላውያን ከግብፅ ወጥተው በምድረ በዳ በተቅበዘበዙ ጊዜ፣ እግዚአብሔር ከሚያስፈልጋቸው በላይ ውሃ አፍልቆ እንደ ሰጣቸው ያመለክታል (ዘፀ 15፥25፡27 ጋር ያነጻጽሩ):: እዚህ ላይ ግን እግዚአብሔር ወደ ፊት የሚፈጽመው የማዳን ሥራው ራሱ፣ እስራኤላውያን ሕይወት ሰጪ የሆነውን ውሃ የሚቀዱበት "ምንጭ" እንደ ሆነ ያመለክታል (መዝ 36፥9፤ ኤር 2፥13፤ ዮሐ 4፥10 ይመ)::

12፥6 *እልል በሉ፤ በደስታም ዘምሩ፤* በ54፥1 ላይ እንደምናየው፣ ጽዮን ሕዝቧ ወደ አገሩ ስለ መመለሱ ከምትገልጸው ደስታ መካከል እነዚህ አባባሎች እንደ ገና ተጠቅሰዋል:: *የእስራኤል ቅዱስ፤* የ1፥4፤ 6፥1 ማብ ይመ::

*13፥1-23፥18፤* በሕዝቦች ላይ የተነገረ ተከታታይ ትንቢት ነው (ኤር 46፥51፤ ሕዝ 25፥32፤ አሞ 1-2፤ ሶፎ 2፥4-15 ይመ):: የእግዚአብሔር ፍርድ በታናናሾቹ ሕዝቦችና መንግሥታት ላይ ከመምጣቱ በፊት በባቢሎን (13፥1-14፥23 ከዚያም በአሦር 14፥24-27) ጀመረ:: እግዚአብሔር በሕዝቡ ላይ ሲፈርድ፣ ጣዖት አምላኪዎችን አይነካቸውም፤ አያገኛቸውም ማለት አይደለም (ኤር 25፥29 ይመ):: በሌላ መልኩ እግዚአብሔር በአሕዛብ ላይ ሲፈርድ ለሕዝቡ መድኀኒት ያመጣል ማለት ነው (ለምሳሌ 10፥12 ይመ)::

*13፥1-14፥27፤* ይህ ትንቢት በአዲሲቱ ባቢሎን ግዛተ ዐፄ የነበረችውን ባቢሎን የሚመለከት ሳይሆን፣ በአሦር ግዛተ ዐፄ ሥር የነበረችውን ባቢሎን የሚመለከት ሳይሆን አይቀርም፤ ስለዚህ ትንቢቱ በቀጥታ የሚመለከተው ባቢሎንን ዋና ከተማው ያደረገውን የአሦርን ግዛተ ዐፄ ነው:: ዓ.ቅ.ክ ከ729 ጀምሮ የአሦር ነገሥታት፣ "የባቢሎን ንጉሥ" የሚል መጠሪያ ነበራቸው::

*13፥1፤* የ1፥1 ማብ ይመ:: *ንግር፤* በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም፣ "ማንሣት፣ መሸከም" ከሚለው ግስ ጋር ይመሳሰላል፤ ስለዚህ በጥቅሉ ሲተረጐም ድምፅን ከፍ አድርጎ መናገር ወይም መሸከም የሚለውን ትርጕም ይሰጣል:: እንዲህ ዐይነቱ ንግር አብዛኛውን ጊዜ የፍርድ መልእክት የያዘ ነው:: *ባቢሎን፤* 21፥1-9፤ 46፥1-2፤ 47፥1-15፤ ኤር 50-51 ይመ:: ፍርዱ የተነገረውም መጀመሪያ በዚያን ጊዜ አሦር ከፈጠረችው ችግር የተነሣ ሲሆን፣ በኋላም ባቢሎን በ605 እና በ586 ዓ.ቅ.ክ ላይ የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን ውድቀት የምታመጣ በመሆኑ ነው:: በ532 ዓ.ቅ.ክ ላይ ባቢሎን በፐርሺያዊው ቂሮስ ተሸነፈች (45፥1፤ 47፥1 ይመ):: ይህም በኋለኛው ጊዜ በእግዚአብሔር መንግሥት ላይ ለሚነሡት የዓለም ኀያላን ትእምርት ሆኖ ቀርቦአል (ከ1ጴጥ 5፥13 ጋር ያነጻጽሩ)፣ የመጨረሻ ውድቀቱም በራእይ 14፥8፤ 16፥19፤ 17-18 ላይ ተነግሮአል፤ እዚህ ላይ ግን ባቢሎን የአሦር ዓፄያዊ መንግሥት አንድ ክፍል ሆና ተቈጥራለች (14፥24-27 እና የ13፥1-14፥27 ማብ ይመ)::

13፥2 *ምልክት ስጡ፤* የ5፥26 ማብ ይመ::

13፥3 *ቅዱሳኔን፤* የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለመፈጸም የተለዩትን ማለት ነው:: አሦርን፣ "በቍጣዬ በትር" ካለበት ከ10፥5 ጋር ያነጻጽሩ፤ 45፥1 ይመ:: *ቍጣዬንም፤* የእግዚአብሔር ቍጣ ከዚያ በኋላ በእስራኤል ላይ አልወረደም (5፥25፤ 9፥12፡17፡21፤ 10፥4 ይመ)፤ የእስራኤልን ጠላቶች ግን አድቅቆአቸዋል (ቍ 5፥9፡13 ይመ፤ ከ30፥27 ጋር ያነጻጽሩ):: እግዚአብሔር ኀጢአትን፣ በተለይም ትዕቢትን መቅጣቱ ተገቢ ነው (ቍ 11 ይመ)::

13፥4 *የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ሰራዊቱን ለጦርነት አሰልፎል፤* እግዚአብሔር የእስራኤል ሰራዊት (1ሳሙ 17፥45)፣ የኀያላን መላእክት (1ነገ 22፥19፤ ሉቃ 2፥13) እና እዚህም ባቢሎንን የሚደመስሰው ሰራዊት አለቃ ነው::

13፥5 *የቍጣው መሣሪያ፤* በኢሳይያስ ዘመን አሦር በእግዚአብሔር እጅ የተያዘ የቅጣት በትር ሲሆን፣ ባቢሎን ራሱም የኋላ ኋላ የእግዚአብሔር ጦር መሣሪያ ሆኖ ያገለግላል (10፥5 እና ማብ ይመ)::

13፥6፡9 *የእግዚአብሔር ቀን፤* የ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ::

13፥7 *እጆች ሁሉ ሽባ ይሆናሉ፤* ድፍረት ያጣሉ ማለት ነው፤ ኤር 6፥24 ይመ::

13፥8 *ሽብር፤* በእግዚአብሔር ቍጣ የሚመጣ ቅዱስ ጦርነት ብዙ ጊዜ በጠላት ላይ ከባድ ድንጋጤ ያመጣል (ዘፀ 15፥14-16፤ መሳ 7፥21-22 ይመ):: *ሥቃይና ... ምጥ፤* ብዙውን ጊዜ ነቢያት በፍርድና በጦርነት የሚመጣውን ሥቃይ ሴት ልትወልድ በምትቃረብበት ሰዓት ከሚያጣድፋት ኀይለኛ ምጥ ጋር ያመሳስሉታል::

[10]የሰማይ ከዋክብትና ሰራዊታቸው፣
ብርሃን አይሰጡም፤
ፀሓይ ገና ከመውጣቷ ትጨልማለች፤
ጨረቃም ብርሃኗን አትሰጥም።
[11]ዓለምን ስለ ክፋቷ፣
ክፉዎችንም ስለ ኀጢአታቸው እቀጣለሁ፤
የትዕቢተኞችን እብሪት እሽራለሁ፤
የጨካኞችንም ጒራ አዋርዳለሁ።
[12]ሰውን ከነጠረ ወርቅ ይልቅ ውድ፣
ከኦፌርም ወርቅ ይበልጥ ብርቅ አደርጋለሁ።
[13]ስለዚህ በሰራዊት ጌታ *በእግዚአብሔር*
*መዓት*፣
ቍጣው በሚነድበት ቀን፣
ሰማያትን እነቀንቃለሁ፤
ምድርንም ከስፍራዋ አናውጣለሁ።

[14]እንደሚታደን ሚዳቋ፣
እረኛም እንደሌለው የበግ መንጋ፣
እያንዳንዱ ወደ ወገኑ ይመለሳል፣
እያንዳንዱም ወደ አገሩ ይሸሻል።
[15]የተማረከ ሁሉ ይወጋል፤
የተያዘም ሁሉ በሰይፍ ይወድቃል።
[16]ዐይናቸው እያየ ሕፃናታቸው ይጨፈጨፋሉ፤
ቤታቸው ይዘረፋል፤ ሚስቶቻቸው
ይደፈራሉ።

[17]እነሆ፤ ለብር ደንታ የሌላቸውን፣
በወርቅም ደስ የማይሰኙትን፣
ሜዶናውያንን አስነሣባቸዋለሁ።
[18]ቀስታቸው ጐበዞችን ይፈጃል፤
ሕፃናትን አይምሩም፤
ዐይናቸውም ለልጆች አይራራም።
[19]የመንግሥታት ዕንቍ፣
የከለዳውያን[a] ትምክሕት፣
የሆነችውን ባቢሎንን፣
*እግዚአብሔር* እንደ ሰዶምና እንደ ገሞራ
ይገለብጣታል።
[20]በዘመናት ሁሉ የሚቀመጥባት አይኖርም፤
የሚቀመጥባትም የለም
ዐረብ በዚያ ድንኳኑን አይተክልም፤
እረኛም መንጋውን በዚያ አያሳርፍም።
[21]ነገር ግን የምድረ በዳ አራዊት በዚያ ይተኛሉ፤
ቀበሮዎች ቤቶቿን ይሞላሉ፤
ጒጒቶች በዚያ ይኖራሉ፤
በበረሓ ፍየል የሚመስሉ አጋንንትም
ይዘለሉበታል።
[22]ጅቦች በምሽጎቿ፣
ቀበሮዎችም በተዋቡ ቤተ መንግሥቶቿ
ይጮኻሉ፤
ጊዜዋ ቀርቦአል፤
ቀኗም አይራዘምም።

# 14

*እግዚአብሔር* ለያዕቆብ ይራራለታል፤
እስራኤልን እንደ ገና ይመርጠዋል፤
በራሳቸውም አገር ያኖራቸዋል።
መጻተኞች አብረዋቸው ይኖራሉ፤
ከያዕቆብም ቤት ጋር ይተባበራሉ።
[2]አሕዛብም ይወስዷቸዋል፤
ወደ ገዛ ስፍራቸውም ይመልሷቸዋል።
የእስራኤል ቤት አሕዛብን ርስት ያደርጋቸዋል፤
*በእግዚአብሔርም* ምድር ወንዶችና ሴቶች
ባሪያዎች አድርገው ይገዟቸዋል፤

13፥10 ዘፀ10፥22፤ ኢዮ9፥7፤ ኢሳ5፥30፤ 24፥23፤ ሕዝ32፥7፤ አሞ5፥20፤8፥9፤ ዘካ14፥7፤ ማቴ24፥29፤ ማር13፥24፤ ራእ8፥12 13፥11 መዝ10፥5፤ 125፥3፤ ምሳ16፥18፤ ኢሳ2፥9፤3፥11፤11፥4፤ 23፥9፤25፥3፡5፤ 26፥21፤29፥5፡20፤ 49፥25፡26፤65፥6-7፤ 66፥16፤ ሕዝ28፥2፤ ዳን4፥37፤5፥23 13፥12 ዘዳ10፥29፤ ኢሳ4፥1 13፥13 ኢዮ9፥5፥6፤ መዝ102፥26፤ ኢሳ9፥19፤14፥16፤ 34፥4፤51፥6፤ ማቴ24፥7፤ ማር13፥8 13፥14 ዘፍ11፥9፤ 1ነገ22፥17፤ ምሳ6፥5፤ ኢሳ17፥13፤21፥15፤ 22፥3፤33፥3፤ ኤር4፥9፤ 46፥16፤50፥16፤51፥9፤ ናሆ3፥7፤ ማቴ9፥36፤ ዮሐ10፥11 13፥15 ኢሳ14፥19፤ ኤር50፥25፤51፥4 13፥16 ቍ18፤ ዘፍ34፥29፤ ዘኍ16፥27፤ 2ነገ8፥12፤ ሆሴ13፥16 13፥17 ቍ3፤ 2ነገ18፥14-16፤ ምሳ6፥34-35፤ ኤር50፥9፡41፤51፥1 13፥18 ቍ16፤ ዘዳ32፥25፤ መዝ7፥12፤ ኢሳ14፥22፤41፥2፤ 47፥6፡9፤ ኤር6፥23፤4 9፥26፤50፥9፡14፡29፡ 30፡42፤51፥4 13፥19 ቍ1፤ ዘፍ19፥25፤ መዝ137፥8፤ ኢሳ1፥9-10፤47፥5፤ ዳን2፥37፡38፤4፥30፤ ሮሜ9፥29፤ ራእ14፥8 13፥20 2ዜና17፥11፤ ኢሳ14፥23፤34፥10-15፤ ኤር51፥29፡37-43፡62 13፥21 ዘሌ11፥16-18፤ 17፥7፤ ዘዳ14፥15-17፤ 2ዜና11፥15፤ መዝ74፥14፤ ኤር14፥6፤ ራእ18፥2 13፥22 ዘዳ32፥35፤ ኢሳ25፥2፤32፥14፤34፥13፡14፤35፥7፤43፥20፤ ኤር9፥11፤48፥16፤49፥33፤50፥39፤51፥33፡37፤ ሚል1፥3 14፥1 ዘፍ18፥19፤ ዘፀ12፥43፤ 2ዜና6፥6፤ መዝ102፥13፤ ኢሳ11፥10፤ 41፥8፤42፥1፤44፥1፤45፥4፤49፥7፡10፡13፤54፥7-8፡10፤65፥9፡22፤ ኤር3፥18፤16፥15፤23፥8፤33፥26፤ ሕዝ47፥22፤ ዘካ1፥17፤2፥12፤3፥2፤ 8፥22-23፤10፥6፤ ኤፌ2፥12-19 14፥2 መዝ49፥14፤149፥8፤ ኢሳ11፥12፤ 26፥15፤43፥14፤45፥14፤49፥7፡23፡25፤54፥3፤60፥9፡12፡14፤61፥5፤ ኤር30፥16፤ 40፥1፤49፥2፤ ሕዝ39፥10፤ ሶፎ3፥19፤ ዘካ2፡9

[a]19 ወይም፣ *ባቢሎናውያን* ማለት ነው።

13፥10 *ከዋክብትና ... ፀሓይ ... ጨረቃም፤* በጠፈር አካላት ላይ የሚፈጠር ጨለማ አብዛኛውን ጊዜ ከጌታ ቀን ጋር ይያያዛል (ኢል 2፥10፡31፤ ራእ 6፥12-13 ይመ፤ ከመሳ 5፥20 ጋር ያነጻጽሩ)።

13፥11 *እብሪት ... ጒራ፤* ከ2፥9፡11፡17፤ 5፥15 ጋር ያነጻጽሩ።

13፥12 *ውድ ... ብርቅ፤* ጦርነት ወንድ ወንዱን ለመጨረስ ጊዜ አይወስድበትም (4፥1 እና ማብ ይመ)። *ከኦፌርም ወርቅ፤* ንጉሥ ሰሎሞን ከዚሁ ቦታ እጅግ ብዙ ወርቅ ያስመጣ ነበር (1ነገ 9፥28፤ 10፥11 እና ማብ ይመ)።

13፥13 *ሰማያትን እነቀንቃለሁ፤ ምድርንም ... አናውጣለሁ፤* የነጐድጓድ ድምፅና የመሬት መንቀጥቀጥ ብዙውን ጊዜ እግዚአብሔር በኀይል መገኘቱን ያመለክታሉ (የቍ 10፤ 34፥4፤ ዘፀ 19፥16 ማብ ይመ)። በረዶም ከእነዚሁ ጋር አብሮ ሊመጣ ይችላል (ከ30፥30፤ ኢሱ 10፥11 ጋር ያነጻጽሩ)።

13፥14 *ይሸሻል፤* ከአሦር ግዛት ለማለት ነው።

13፥16 *ሕፃናታቸው ይጨፈጨፋሉ፤* ወራሪው ሰራዊት ሕፃናትንና ልጆችንም ጭምር ስለሚፈጅ፣ የሚዋጋ ተተኪ ትውልድ አይኖርም፤ በከተማዪቱም የሰው ዘር አይታይባትም (መዝ 137፥8-9፤ ሆሴ 10፥14፤ ናሆ 3፥10)። *ሚስቶቻቸው ይደፈራሉ፤* ሴቶችም እንደዚሁ ጦርነት ጊዜ በእጅጉ ይሠቃያሉ። ባሎቻቸው ስለሚገደሉ እንደ ሴትኛ ዐዳሪ ይሆናሉ (የአሞ 7፥17 ማብ ይመ)።

13፥17 *ሜዶናውያንን፤* ዛሬ ቦታው በሰሜን ምዕራብ ኢራን ውስጥ ይገኛል። ሰምንት መቶ ዓ.ቅ.ክ ላይ በአሦርና በምድያም መካከል ግጭት ተፈጥሮ ነበር፤ አንዳንዶች ግን የዚህን ትንቢት መፈጸም የሚያያይዙት ሜዶናውያን ከባቢሎናውያን ጋር በመተባበር በ612-609 ዓ.ቅ.ክ ካሸነፉበት በኋላም ዳግመኛ ከቂሮስ ጋር አንድ ሆነው በ539 ዓ.ቅ.ክ ላይ ባቢሎንን ድል ካደረጉበት ጊዜ ጋር ነው (ኤር 51፥11፡28፤ ዳን 5፥31፤ 6፥28 ይመ)።

13፥19 *ትምክሕት፤* ባቢሎን በቤተ ጣዖቶቿና በቤተ መንግሥቷ ሕንጻዎች፣ እጅግ ውብ ከተማ ሆነች (ዳን 4፥29-30 ይመ)። ሰገነት ላይ የሚገኘው የናቡከደነፆር የአትክልት ስፍራ ጥንታዊ ከሆኑ ሰባት የዓለም አስደናቂ ነገሮች አንዱ ነው። *የከለዳ ውያን፤* የአዲሲቱ የባቢሎን መንግሥት ከ612-539 ዓ.ቅ.ክ ላይ ከደቡባዊው ባቢሎን በመጡ ከለዳውያን ይመራ ነበር። በ626 ዓ.ቅ.ክ አካባቢ፣ ናቦፖላሳር ተለያይተው የነበሩትን ነገዶች አንድ አደረጋቸው፤ ልጁም ናቡከደነፆር መሪያቸው ሆነ (ዘመኑ 605 ዓ.ቅ.ክ ነው)። እንደ ሰዶምና እንደ ገሞራ ቀደም ሲል ኢሳይያስ እነዚህን ከተሞች ከይሁዳ ጋር አነጻጽሮአቸዋል (1፥9-10 እና ማብ ይመ)።

*13፥20-22፤* በ34፥10-15 ላይ የኤዶምን ባድማነት በማስመልከት የቀረበውን ተመሳሳይ ዝርዝር መግለጫ ይመ፤ ከራእ 18፥2 ጋር ያነጻጽሩ።

13፥20 *የሚቀመጥባት አይኖርም፤* ባቢሎን ከክርስቶስ ልደት በኋላ በሰባተኛው ምእተ ዓመት ፈጽሞ ሰው የማይኖርባት ምድረ በዳ ሆና ነበር።

13፥21 *በበረሓ ፍየል፤* ይህ ስም ከአጋንንት ጋር የተያያዘ ነው፤ ዘሌ 17፥7፤ 2ዜና 11፥15 ይመ። በራእ 18፥2 ላይ የወደቀችው ባቢሎን የአጋንንትና የክፉ መናፍስት መኖሪያ መሆኗ ተገልጾአል።

14፥1 *ይራራለታል ... ያኖራቸዋል፤* የባቢሎን መውደቅ ከእስራኤል መንግሥት ዳግም ምሥረታ ጋር የተያያዘ ነው። እግዚአብሔር ለሕዝቡ ምሕረት የማድረጉ ነገር ከምዕራፍ 40-66 ባለው ክፍል መሪ ሐሳብ ሆኖ ቀርቦአል (40፥1-2 ይመ)። *በራሳቸውም አገር፤* 2፥2-4፤ 11፥10-12 እና ማብ ይመ። *መጻተኞች አብረዋቸው ይኖራሉ፤* 11፥10፤ 56፥6-7፤ 60፥3 ይመ።

14፥2 *አሕዛብም ... ስፍራቸው፤* የ5፥26 ማብ ይመ። *አሕዛብን ርስት ያደርጋቸዋል፤* የ11፥14 ማብ ይመ።

የማረኳቸውን ይማርኳቸዋል፤
 የጨቈኗቸውንም ይገዟቸዋል።

[3]እግዚአብሔር ከሥቃይህ፣ ከመከራህና ከጽኑ ባርነትህ ባሳረፈህ ቀን፣ [4]በባቢሎን ንጉሥ ላይ ትሣለቃለህ፤ እንዲህም ትላለህ፤

 ጨቋኙ እንዴት አበቃለት!
 አስገባሪነቱስ[ሩ] እንዴት አከተመ!
[5]እግዚአብሔር የክፉዎችን ዘንግ፣
 የገዦችንም በትረ መንግሥት ሰብሮአል፤
[6]ሕዝቦችን በማያቋርጥ ቍጣ የመታውን፣
 ያለ ርኅራኄ እያሳደደ
 የቀጠቀጠውን ሰብሮአል።
[7]ምድር ሁሉ ሰላምና ዕረፍት አገኘች፤
 የደስታም ዝማሬ ታስተጋባለች።
[8]ጥድና የሊባኖስ ዝግባ እንኳ ደስ ብሎአቸው፣
 "አንተም ወደቅህ፤
ዕንጨት ቈራጭም
 መጥረቢያ አላነሣብንም" አሉ።

[9]በመባህ ጊዜ
 ሲኦል[T] ልትቀበልህ ተነሣሥታለች፤
ይቀበሉህም ዘንድ የሙታንን መናፍስት፣
 በዓለም ገዥ የነበሩትን ሁሉ ቀስቅሳለች፤
በአሕዛብ ላይ የነገሡትን ነገሥታት
 ከዙፋናቸው አውርዳለች።
[10]እነርሱ ሁሉ ይመልሱልሃል፤
 እንዲህም ይሉሃል፤
"አንተም እንደ እኛ ደከምህ፤
 እንደ እኛም ሆንህ።"
[11]ክብርህ፣ ከነበገና ድምፁ
 ወደ ሲኦል ወረደ፤
ብሎች ከበታችህ ተነጥፈዋል፤
 ትሎችም መደረቢያህ ይሆናሉ።

[12]አንተ የንጋት ልጅ፣ አጥቢያ ኮከብ ሆይ፤
 እንዴት ከሰማይ ወደቅህ!
አንተ ቀድሞ መንግሥታትን ያዋረድህ፤
 እንዴት ወደ ምድር ተጣልህ!
[13]በልብህም እንዲህ አልህ፤
 "ወደ ሰማይ ዐርጋለሁ፤
ዙፋኔንም
 ከእግዚአብሔር ከዋክብት በላይ ከፍ አደርጋለሁ፤
በተራራው መሰብሰቢያ፣
 በተቀደሰውም ተራራ[ሀ] ከፍታ ላይ በዙፋኔ
  እቀመጣለሁ፤
[14]ከደመናዎችም ከፍታ በላይ ዐርጋለሁ፤
 ራሴንም እንደ ልዑል አደርጋለሁ።"
[15]ነገር ግን ወደ ሲኦል፣
 ወደ ጥልቁም ጕድጓድ ወርደሃል።

[16]የሚያዩህም አትኵረው እየተመለከቱህ፣
 በመገረም ስለ አንተ እንዲህ ይላሉ፤
"ያ ምድርን ያናወጠ፣
 መንግሥታትን ያንቀጠቀጠ፣ ይህ ሰው ነውን?
[17]ዓለምን ምድረ በዳ ያደረገ፤
 ከተሞችን ያፈራረሰ፣
 ምርኮኞቹንም ወደ አገራቸው እንዳይሄዱ
  የከለከለ ይህ ነውን?"

[18]የአሕዛብ ነገሥታት ሁሉ በክብር አንቀላፍተዋል፤
 በየመቃብራቸው ዐርፈዋል።
[19]አንተ ግን እንደማይፈለግ ቅርንጫፍ፣
 ከመቃብር ወጥተህ ተጥለሃል፤
በሰይፍ በተወጉት፣
 ወደ ጥልቁ ድንጋዮች በወረዱት፣

14፥3 ዘፀ1፥14፤ ኢዮ3፥17፤ ኢሳ11፥10
14፥4 ኢሳ9፥4፤ 13፥1፤ሚክ2፥4፤ዕን2፥6
14፥5 መዝ110፥2፤ 125፥3፤ኢሳ10፥15
14፥6 2ነገ15፥29፤ መዝ47፥3፤ ኢሳ10፥14፤47፥6፤ ዕን1፥17
14፥7 ዘኍ6፥26፤ መዝ98፥1፤126፥1-3፤ ኢሳ12፥6፤ኤር50፥34፤ ዘካ1፥11
14፥8 2ነገ19፥23፤ 1ዜና16፥33፤ መዝ65፥13፤ ኢሳ37፥24፤ሕዝ31፥16
14፥9 ኢዮ3፥14፤ 26፥5፤ምሳ30፥16፤ ሕዝ32፥21፤ዘካ10፥3
14፥10 ሕዝ26፥20፤ 32፥21
14፥11 ዘኍ16፥30፤ ኢዮ7፥5፤21፥26፤ 24፥20፤ምሳ30፥16፤ ኢሳ5፥12፤51፥8፤ 66፥24፤ሕዝ26፥13፤ አሞ6፥5
14፥12 ሕዝ26፥17፤ ሉቃ10፥18፤ 2ጴጥ1፥19፤ራእ2፥28፤ 8፥10፤9፥1
14፥13 መዝ82፥1፤ ኢሳ37፥24፤ሕዝ28፥2፤ ዳን5፥23፤8፥10፤ አብ1፥4፤ማቴ11፥23፤ 2ተሰ2፥4
14፥14 ዘፍ3፥5፤ ዘኍ24፥16፤ኢዮ20፥6፤ ኢሳ10፥13፤47፥8፤ ኤር50፥29፤51፥53፤ ዳን11፥36፤2ተሰ2፥4
14፥15 ኢዮ21፥13፤ መዝ55፥23፤ኢሳ13፥6፤ 45፥7፤47፥11፤ ኤር51፥8፡43፤ ሕዝ31፥16፤32፥23፤ ማቴ11፥23፤ ሉቃ10፥15
14፥16 ኢሳ2፥19፤13፥13፤ኤር50፥23፤ኢል3፥16፤ሐጌ2፥6፡21፤ ራእ18፥9 14፥17 ዘፀ7፥14፤2ነገ15፥29፤መዝ52፥7፤ኢሳ15፥6፤ ኤር50፥33፤ኢል2፥3፤ራእ18፥18 14፥18 ኢዩ21፥32
14፥19 ኢሳ13፥15፤22፥16-18፤34፥3፤ኤር8፥1፤36፥30፤41፥7-9

[ሩ]4 የሙት ባሕር ጥልቅ፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጒምና የሱርስቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ ነገር ግን በማሶሬቱ ቅጅ የቃሉ ትርጒም በትክክል አይታወቅም።
[T]9 በዚህና በቍጥር 11 እንዲሁም 15 ላይ አንዳንድ ቅጆች፣ መቃብር ይላሉ።
[ሀ]13 ወይም ሰሜን፤ በዕብራይስጡ፣ ዛፎን ተብሎ መተርጐም ይችላል።

*14፥3-21፤* የባቢሎን ንጉሥ ራሱን ከፍ ከፍ አድርጎ በማየት እንደ አምላክ ለመሆን መንጠራራት ቢያምረውም (ቍ. 12-14 ይመ)፣ የዓለም መሪዎች ሁሉ ወደሄዱበት መቃብር ከመውረድ አልዳነም።

14፥3 *ከሥቃይህ ... ከጽኑ ባርነትህ፤* የባቢሎን ምርኮ እስራኤል በምድረ ግብፅ ከነበሩበት የባርነት አገዛዝ ከባድ ቀንበር ጋር ባብዛኛው የሚመሳሰል ነበር (ከዘፀ 1፥14 ጋር ያነጻጽሩ)።

14፥4 *በባቢሎን ንጉሥ፤* ለአሦር ንጉሥ የተሰጠ ሌላ ስም ነው። *ትሣለቃለህ፤* በራእ 18 እንደ ተጻፈው በባቢሎን ላይ ከተደረገው ሥላቅ ጋር ያነጻጽሩ።

14፥5 *ዘንግ ... በትረ መንግሥት፤* 10፥5 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 10፥24 ይመ።

14፥7 *ዝማሬ ታስተጋባለች፤* 12፥6 እና ማብ ይመ።

14፥8 *ጥድና ... ዝግባ፤* ኢሳይያስ አብዛኛውን ጊዜ ተፈጥሮን በሰውኛ ዘይቤ ይገልጻል። በ44፥23 ላይ ዛፎች ከተራሮች ጋር እንደ ዘመሩ ተጠቅሶአል (ከ55፥12 ጋር ያነጻጽሩ)። *የሊባኖስ ዝግባ፤* እጅግ ውድ የሆኑትን እነዚህን ዛፎች የባቢሎንና የአሦር ነገሥታት ለብዙ መቶ ዓመታት ሲያግዟቸው ኖረዋል።

14፥9 *ገዥ፤* በቁሙ፣ "ፍየሎች" ማለት ነው። ፍየል ብዙውን ጊዜ የበግን መንጋ መርቶአል (ኤር 50፥8 ይመ)። በዘካ 10፥3 ላይም ቃሉ፣ "እረኞች" ከሚለው ጋር ተያይዞ ይገኛል። *ከዙፋናቸው አውርዳለች፤* በሙታኑ መካከል ያሉት ሁኔታዎች፣ በምድር ላይ በነበሩበት ጊዜ ከፈጸሟቸው ተግባሮች ጋር ተያይዘው በግልጽ ተቀምጠዋል።

14፥11 *ክብርህ ... ሲኦል፤* ከ5፥14 ጋር ያነጻጽሩ። *ከነበገና ድምፁ፤* ሙዚቃ አንዳንድ ጊዜ የተድላና የደስታ ምልክት ነው (አሞ 6፥5-6)።

*14፥12-15፤* አንዳንዶች ይህ ክፍል ኢሳይያስ የሰይጣንን አወዳደቅ አስመልክቶ የገለጸበት ስፍራ እንደ ሆነ (ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዚች ምድር ላይ በነበረበት ዘመን ይህንኑ ድርጊት ከራሱ ጋር አያይዞ ከጠቀሰበት ከሉቃ 10፥18 ጋር ያነጻጽሩ)ያምናሉ። ምንባቡ በግልጽ የሚያመለክተው ግን በኋለኛው ዘመን፣ "አውሬው" በመባል የመጨረሻውን ዘመን ባቢሎን ለሚመራው ምሳሌ ሆኖ የቀረበውን (ራእ 13፥4፡ 17፥3 ይመ) የባቢሎን ንጉሥ ነው። በሕዝ 28 የጢሮስ ገዥ ከተገለጠበት ማብራሪያ ጋር ያነጻጽሩ።

14፥12 *አጥቢያ ኮከብ፤* ይህ ቃል ከዕብራይስጥ ወደ ሮማይስጥ (ላቲን) ቋንቋ ሲመለስ፣ "ሉሲፈር" የሚል ትርጒም ተሰጥቶታል።

14፥13 *በተቀደሰውም ተራራ፤* የዛፎን ተራራ (መዝ 48፥1-2 ይመ) ወይም የካስየስ ተራራ ይባላል፤ በሶርያ ኡጋሪት ከሚባለው ስፍራ በስተ ሰሜን ምሥራቅ 40 ኪሎ ሜትር ያህል ይርቃል። ግሪኮች ስለ ኦሊምፐስ ተራራ እንደሚያስቡት፣ ከነዓናውያን ተራራውን የአማልክት መኖሪያና መገናኛ ቦታ ነው ብለው ያስቡ ነበር (መዝ 48፥2 እና ማብ ይመ)፤ ከመዝ 82፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

*14፥16-20፤* እነዚህ ጥቅሶች በሙታኑ ዓለም በሲኦል ያለውን ሁኔታ ሳይሆን፣ በምድር የሚፈጸመውን የሚገልጹ ይመስላሉ (ምናልባት ደግሞ ቍ. 9-10 ይመ)።

14፥17 *ምርኮኞቹንም ወደ አገራቸው እንዳይሄዱ፤* ልክ እንደ አሦራውያን ሁሉ፣ ባቢሎናውያንም በመካከላቸው ያሉትን ዐመፀኞች ቅስም ለመስበር ካሸነፉት ሕዝብ የተወሰነውን ወደ ሌላ ስፍራ ያግዙ ነበር (2ነገ 24፥14-16 ይመ)።

14፥19 *ከመቃብር ወጥተህ ተጥለሃል፤* ተገቢ የሆነ የቀብር ሥነ ሥርዐት ለማንኛውም ሰው፣ በተለይም ለንጉሥ ይደረግ ነበር።

በተገደሉትም ተሸፍነሃል።
እንደ ተረገጠም ሬሳ ሆነሃል።
[20]ከእነርሱ ጋር በመቃብር አትሆንም፤
ምድርህን አጥፍተሃልና፤
ሕዝብህንም ፈጅተሃልና።

የክፉ አድራጊዎች ዘር
ፈጽሞ አይታወስም።
[21]ተነሥተው ምድርን እንዳይወርሱ፣
ዓለምንም በከተሞቻቸው እንዳይሞሉ፣
ስለ አባቶቻቸው ኀጢአት፣
ወንድ ልጆቹ የሚታረዱበትን ስፍራ አዘጋጁ።
[22]"በእነርሱ ላይ እነሣለሁ"
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር።
"ስሚንና ትሩፋኖቿን፣
ዘሯንና ትውልዷን ከባቢሎን እቈርጣለሁ"
ይላል እግዚአብሔር።
[23]"የጃርት መኖሪያ፣
ረግረጋማ ቦታ አደርጋታለሁ፤
በጥፋትም መጥረጊያ እጠርጋታለሁ"
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር።

## በአሦር ላይ የተነገረ ትንቢት

[24]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ብሎ ምሎአል፤
"እንደ ዐቀድሁት በእርግጥ ይከናወናል፤
እንደ አሰብሁትም ይሆናል።
[25]አሦርን በምድሬ ላይ አደቃለሁ፤
በተራራዬም ላይ እረግጠዋለሁ፤
ቀንበሩ ከሕዝቤ ላይ ይነሣል፤
ሸክሙም ከትከሻቸው ላይ ይወርዳል።"

[26]ለምድር ሁሉ የታሰበው ዕቅድ ይህ ነው፤
በአሕዛብም ሁሉ ላይ የተዘረጋው እጅ ይኸው ነው።
[27]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ አስቦአል፤
ማንስ ያግደዋል?
እጁም ተዘርግቶአል?
ማንስ ይመልሰዋል?

## በፍልስጥኤማውያን ላይ የተነገረ ትንቢት

[28]ንጉሡ አካዝ በሞተበት ዓመት እንዲህ የሚል ንግር መጣ፤
[29]"እናንት ፍልስጥኤማውያን ሆይ፤
የመታችሁ በትር ስለ ተሰበረ ሁላችሁ ደስ አይበላችሁ፤
ከእባቡ ሥር እፉኝት ይወጣልና፤
ፍሬውም ተወርዋሪ መርዘኛ እባብ ይሆናል።
[30]ከድኾም ድኻ የሆኑት መሰማሪያ ያገኛሉ፤
ችግረኞችም ተዝናንተው ይተኛሉ፤
ሥርህን ግን በራብ እገድላለሁ፤
ትሩፋንህንም እፈጃለሁ።

[31]በር ሆይ፣ ዋይ በል፤ ከተማ ሆይ ጩኽ፣
ፍልስጥኤማውያን ሆይ፤ ሁላችሁም በፍርሀት ቅለጡ!
ጢስ ከሰሜን መጥቶብሃል፤
ከሰልፉ ተነጥሎ የሚቀር የለምና።
[32]ከዚያ ሕዝብ ለሚመጡ መልእክተኞች
ምን መልስ ይሰጣል?
መልሱ፣ "እግዚአብሔር ጽዮንን መሥርቶአል፤
መከራን የተቀበለው ሕዝብም፣
በእርሷ ውስጥ መጠጊያን አግኝቶአል"
የሚል ነው።

## በሞዓብ ላይ የተነገረ ትንቢት

**15** ስለ ሞዓብ የተነገረው ንግር ይህ ነው፤
የሞዓብ ዔር ፈራረሰች፤
በአንድ ሌሊትም ተደመሰሰች።
የሞዓብ ቂር ፈራረሰች፣

14፥20 ዘዳ32፥26፤ 1ነገ21፥19፤ኢዮ18፥19፤ ኢሳ1፥4
14፥21 ዘፍ9፥25፤ ዘሌ26፥39፤ ዘኍ16፥27
14፥22 2ሳሙ18፥18፤ 1ነገ14፥10፤ኢዮ18፥17፥19፤መዝ9፥6፤94፥16፤109፥13፤ኢሳ13፥18፤ ናሆ1፥14
14፥23 ዘሌ11፥16-18፤ኢሳ10፥3፤ 34፥11-15፤ኤር25፥12፤ 50፥3፤51፥62፤ ሶፎ2፥14
14፥24 ኢዮ9፥3፤ ኢሳ7፥7፤19፥12፥17፤ 23፥8-9፤25፥1፤ 45፥23፤46፥10-11፤ 49፥18፤54፥9፤62፥8፤ ሕዝ12፥25፤ዳን4፥35፤ ሐሥ4፥28
14፥25 ኢሳ9፥4፤ 10፥5፥12፥27፤ 37፥36-38
14፥26 ዘፀ15፥12፤ ኢዮ30፥21፤ኢሳ23፥9
14፥27 ዘፀ14፥21፤ 2ዜና20፥6፤ኢሳ43፥13፤ ኤር49፥20፤ዳን4፥35
14፥28 2ነገ15፥7፤ 16፥1፤ኢሳ13፥1
14፥29 ዘዳ8፥15፤ ኢሳ13፥3፤2ነገ1፥2፤ 2ዜና26፥6፤ኢሳ11፥8
14፥30 ኢሳ3፥15፤ 7፥21-22፤8፥21፤ 9፥20፤25፥4፤51፥19፤ ኤር25፥16፤ ሕዝ25፥15-17፤ ሶፎ2፥5፤ዘካ9፥5-6
14፥31 ዘፍ10፥14፤ ኢሳ3፥26፤5፥27፤ 13፥6፤41፥25፤ ኤር1፥14፤4፥6፤6፥1፥22፤10፥22፤13፥20፤ 25፥9፤46፥20፥24፤ 47፥2፤50፥41፤ ሕዝ32፥30
14፥32 መዝ51፥18፤87፥2፥5፤ኢሳ2፥2፤4፥6፤26፥1፤ 28፥16፤31፥5፤33፥5፥20፤37፥9፤44፥28፤51፥21፤54፥11፤ያዕ2፥5
15፥1 ዘኍ17፥12፤21፥15፤22፥3-6፤ዘዳ23፥6፤2ነገ3፥25፤ኢሳ11፥14፤ 13፥1፤ 25፥12፤26፥5፤ኤር48፥24፥41፤51፥58

የሰው አስከሬን ከመቃብሩ ወጥቶ የትም እንዲጣል ማድረግ አስከፊ ነው። *እንደ ተረገጠም ሬሳ ሆነሃል፤* 5፥25 ይመ።

14፥21 *ወንድ ልጆቹ የሚታረዱበትን፤* ለሰው ልጆቹ እንዲሁም የመቃብር ሐውልቱ መታሰቢያዎቹ ናቸው (ከ2ሳሙ 18፥18 ጋር ያነጻጽሩ)። የባቢሎን ንጉሥ ግን አንዱም አይኖረውም (ከ47፥9 ጋር ያነጻጽሩ)።

*14፥22-23፤* የመሣለቂያው ቃል ባቢሎንንም ለመጨመር ሰፋ እንዲል ተደርጎአል (የቍ 3-21 ማብ ይመ)፤ ይህ ሰናክሬም በ689 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎንን በደመሰሰ ጊዜ በከፊል፣ በኋላም ሜዶንና ፋርስ በ539 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎንን በያዙ ጊዜ ሙሉ በሙሉ ተፈጽሞአል።

14፥22 *ትሩፋኗን፤* በሕይወት የተረፉ እስራኤላውያን ቅሬታ ሆነው ይኖራሉ (10፥20-22፤11፥11፥16 ይመ)፤ ባቢሎናውያን ግን በሕይወት የሚተርፍ ቅሬታ አይኖራቸውም።

*14፥23፤* 13፥20-22 እና ማብ ይመ። *ረግረጋማ ቦታ፤* ደቡባዊ ባቢሎን፣ ከለዳውያን የኖሩበት ረግረግ ያለበት ስፍራ ነው።

*14፥24-27፤* ሶፎ 2፥13-15 ይመ፤ የ13፥1-14፥27 ማብ ይመ።

14፥24 *ይሆናል፤* 8፥10 እና ማብ ይመ። አሦርንና ባቢሎንን በተመለከተ የተነገረው መጨረሻው የእግዚአብሔር ዕቅድ ይፈጸማል።

14፥25 *ቀንበሩ ... ሸክሙም፤* 9፥4 እና ማብ ይመ።

14፥26-27 *የተዘረጋው እጅ፤* 9፥12፤ 12፥1 እና ማብ ይመ። በቀይ ባሕር የእግዚአብሔር እጅ በግብፃውያን ላይ ተዘርግቶ ነበር (ዘፀ 15፥12 ይመ)።

*14፥28-32፤* ኤር፤ 47፤ ሕዝ 25፥15-17፤ አሞ 1፥6-8፤ ሶፎ 2፥4-7 ይመ።

14፥28 *በሞተበት ዓመት፤* ምናልባት 715 ዓ.ቅ.ክ ይሆናል። ይህ ሁኔታ የተፈጸመው ንጉሥ ሳርጎን (20፥1 ይመ) የተነሣበትን ዐመፅ ለመግታት በውጥር ተይዞ ፊቱን ወደ ከነዓን ለማዞር ባሰበበት ጊዜ፣ ፍልስጥኤማውያን በአሦራውያን ላይ ያመፁበት ወቅት ነበር። *ንግር፤* የ13፥1 ማብ ይመ።

14፥29 *ፍልስጥኤማውያን፤* የዘፍ 10፥14 ማብ ይመ። ከግብፅ ወደ መስጴጦምያ በሚወስደው መንገድ ላይ የተዘረጋ ስለ ነበር፤ የፍልስጥኤም ግዛት በታላላቅ መንግሥታት (በግብፅና በአሦር) በቀላሉ ለመጠቃት የተጋለጠ ነበር። *በትር፤* ምናልባት የአሦርን ንጉሥ ሳርጎንን ይመለከታል። *ስለ ተሰበረ፤* በትሩ ንጉሥ ሳርጎን ከሆነ፣ መሰበሩ የሚያመለክተው በግዛቱ በባቢሎንና በትንሹ እስያ የሚነሣው ተከታታይ ዐመፅ ለመንግሥቱ አስጊ መሆኑን ነው። *ሥር ... ፍሬውም፤* ሙሉውን ዛፍ በተመለከተ ወደ ታች ጥልቀቱን፣ ወደ ላይ ምጥቀቱን ለመግለጥ በዘይቤያዊ አገላለጽ የቀረበ አባባል ነው። ከሳርጎን በኋላ ሌሎች የአሦር ነገሥታት ይመጣሉ፤ እነርሱም ሰናክሬም፣ አስራዶንና አሹርባኒፓል ናቸው።

14፥30 *ድኻ ... ችግረኞችም፤* እስራኤላውያንን ለማለት ነው (ቍ 32 ይመ)።

14፥31 *ዋይ በል፤* በ13፥6፤ 15፥2፤ 16፥7፤ 23፥1 ላይ ከተጠቀሰው ተመሳሳይ ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ። *ጢስ፤* ከሰሜን እየተነሡ ምድሪቱን በተደጋጋሚ ይወጉ የነበሩት የአሦር ሰራዊትና ሠረገሎች እግር የሚያነሣውን ትቢያ ለማመልከት ነው። *ተነጥሎ የሚቀር፤* በ5፥26-29 ላይ በሰፊው ተገልጾአል።

14፥32 *ጽዮንን መሥርቶአል፤* እግዚአብሔር ኢየሩሳሌምን ከአሦራውያን ወረራ ይጠብቃል (31፥4-5 ላይ ያለውን ከ2፥2 ጋር ያነጻጽሩ)።

*15፥1-16፥14፤* ኤር 48፤ ሕዝ 25፥8-11፤ አሞ 2፥1-3፤ ሶፎ 2፥8-11 ይመ።

15፥1 *ሞዓብ፤* ከሙት ባሕር በስተ ምሥራቅ የሚገኝ አገር ሲሆን፣ የእስራኤል የምንጊዜውም ጠላቷ ነው (25፥10፤ 2ነገ 13፥20

በአንድ ሌሊት ተደመሰሰች፡፡
[2]ዲቦን ወደ መቅደሱ ወጣ፤
ሊያለቅስም ወደ ኰረብታው ሄደ፤
ሞዓብ ስለ ናባው፣ ስለ ሜድባም ዋይታ
ያሰማል፤
ራስ ሁሉ ተመድምዶአል፤
ጢምም ሁሉ ተላጭቶአል፡፡
[3]በየመንገዱም ማቅ ይለብሳሉ፤
በየሰገነቱና በየአደባባዩ
ሁሉም ያለቅሳሉ፤
እንባም ይራጫሉ፡፡
[4]ሐሴቦንና ኤልያሊ ጮኹ፤
ድምፃቸው እስከ ያሀድ ድረስ ተሰማ፤
ስለዚህ የሞዓብ ጦረኞች ጮኹ፤
ልባቸውም ራደ፡፡

[5]ልቤ ስለ ሞዓብ አለቀሰ፤
ስደተኞቿም እስከ ዞዓር፣
እስከ ዔግላት ሺሊሺያ ሸሹ፤
እንባቸውን እያፈሰሱ፣
ወደ ሉሒት ወጡ፤
በሖሮናይም መንገድም፣
ስለ ጥፋታቸው ዋይ እያሉ ነጕዱ፡፡
[6]የኔምሬ ውሆች ደርቀዋል፤
ሣሩ ጠውልጎአል፤
ቡቃያውም ጠፍቶአል፤
ለምለም ነገር አይታይም፡፡
[7]ስለዚህ ያገኙትን ሀብት፣
ያከማቹትን ንብረት ከአኻያ ወንዝ ማዶ
ተሸክመው ያሻግሩታል፡፡
[8]ጩኸታቸው እስከ ሞዓብ ዳርቻ ድረስ
ያስተጋባል፤
ዋይታቸው እስከ ኤግላይም፣
ሰቈቃቸውም እስከ ብኤርኢሊም ደረሰ፡፡
[9]የዲሞን[^] ወንዞች በደም ተሞልተዋል፤
በዲሞን ላይ ግን ከዚያ ነገር የበለጠ
አመጣለሁ፤
ከሞዓብ በሚሸሹት፣
በምድሪቱም ላይ በሚቀሩት አንበሳ
እሰድዳለሁ፡፡

16 ከምድረ በዳው ማዶ ካለችው ከሴላ፣
ለምድሪቱ ገዥ፣
ወደ ጽዮን ሴት ልጅ ተራራ
የበግ ጠቦት ግብር ላኩ፡፡
[2]ከጐጆአቸው ተባርረው
ግራ እንደ ተጋቡ ወፎች፣
የሞዓብ ሴቶችም
በአርኖን ወንዝ መሻገሪያ እንዲሁ ይሆናሉ፡፡
[3]"ምክር ለግሱን፤
ውሳኔ ስጡን፤
በቀትር ጥላችሁን
እንደ ሌሊት አጥሉብን፤
የሸሹትን ደብቁ፤
ስደተኞችን አሳልፋችሁ አትስጡ፡፡

15፥2 ዘሌ13፥40፤ ዘኍ21፥30፤32፥38፤ 2ሳሙ10፥4፤ 1ነገ11፥7፤ኢዮ1፥20፤ ኢሳ13፥6፤16፥12፤ 65፥14፤ኤር48፥35
15፥3 ቍ5፤ ኢሱ2፥8፤ኢሳ3፥24፤ 14፥31፤16፥9፤22፥4፤ ኤር47፥2፤48፥38፤ ሰቆ2፥11፤ሕዝ7፥18፤ ሚክ1፥8
15፥4 ዘኍ21፥23፡ 25፤32፥3፤ኢሱ13፥26
15፥5 ቍ3፤ ዘፍ13፥10፤ ዘኍ21፥29፤ኢሳ16፥11፤ ኤር4፥20፤48፥31፡34
15፥6 መዝ37፥2፤ ኢሳ14፥17፤16፥8፤ 19፥5-7፤24፥4፡7፡11፤ 33፥9፤34፥4፤37፥27፤ 40፥7፤51፥6፡12፤ ኤር14፥5፤48፥34፤ ሆሴ4፥3፤ኢል1፥12
15፥7 ኢሳ30፥6፤ ኤር48፥36
15፥8 ዘኍ21፥16
15፥9 2ነገ17፥25፤ ሕዝ25፥8-11
16፥1 መሳ1፥36፤ 2ነገ3፥4፤2ዜና32፥23፤ ኢሳ10፥32፤አብ3
16፥2 ዘኍ21፥13-14፡ 29፤መሳ12፥5፤ ምሳ27፥8፤ኤር48፥20
16፥3 1ነገ18፥4

[^]9 የማሶሬቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሙት ባሕር ጥቅል፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕምና የቡልጌት ቅጅ ግን፣ *ዲቦን* ይላሉ፡፡

ይመ)፡፡ *ንገር፤* የ13፥1 ማብ ይመ፡፡ *ዔር፤* ይህ ከተማ የት እንደ ሆነ አይታወቅም፡፡ *ፈራረሰች፤* በ6፥5 ላይ ይህ ቃል ኢሳይያስ ስለ ራሱ የተሰማውን ስሜት ይገልጻል፡፡ የሞዓብ መደምሰስ ምናልባትም በ715 ወይም በ713 ዓመት ዓ.ቅ.ክ የአሦር ንጉሥ ሳርጎን ካካሄደው ወረራ ጋር የተያያዘ ሳይሆን አይቀርም፤ ከኤር 48፥1-17 ጋር ያነጻጽሩ፡፡ *ቂር፤* ምናልባት ከአርኖን ወንዝ በስተ ደቡብ 24 ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ የምትገኝ፣ በዚያን ጊዜ የሞዓብ ዋና ከተማ የነበረችው ቂር ሐርሰት ሳትሆን አትቀርም፡፡ "ቂር" ማለት ከተማ ማለት ነው፡፡

15፥2 *ዲቦን፤* ከአርኖን ወንዝ 6 ኪሎ ሜትር በስተ ሰሜን በኩል የሚገኝና በአንድ ወቅት ለጋድ ነገድ የተሰጠ ነበር (ዘኍ 32፥34 ይመ)፡፡ *ኰረብታው፤* ማምለኪያ ስፍራዎች አብዛኛውን ጊዜ በኰረብታ ዐናት ላይ ይሠራሉ፤ ይህም ከጣዖት አምልኮ ጋር የተያያዘ ነው፡፡ *ናባው፤* ከአርኖን ወንዝ በስተ ሰሜን የሚገኝ ሲሆን፣ ምናልባትም ከናባው ተራራ አጠገብ የሚገኝ ነው (ዘዳ 34፥1)፡፡ *ሜድባ፤* ከሐሴቦን በስተ ደቡብ 9 ኪሎ ሜትር ያህል (ቍ 4 ይመ) የሚርቅ ሲሆን፣ አንድ ጊዜ እስራኤላውያን ከንጉሥ ሴዎን በወረራ ይዘውት ነበር (ዘኍ 21፥26፡30 ይመ)፡፡ *ራስ … ተመድምዶአል፤ ጢምም … ተላጭቶአል፤* የከባድ ሐዘን መግለጫ ምልክት ነው (ኤር 48፥37)፡፡

15፥3 *ማቅ፤* ሐዘንተኞች የሚለብሱት ከፍየል ጠጕር የሚሠራ ሻካራ በርኖስ ነው (ኢዮ 16፥15፤ ኤር 48፥37፤ ሰቆ 2፥10 ይመ)፡፡ *በየሰገነቱ፤* የተመረጠበት ምክንያት ምናልባት ዕጣን በዚያ ስለሚቀርብ ሊሆን ይችላል (ኤር 19፥13 ይመ)፡፡

15፥4 *ሐሴቦን፤* ከሙት ባሕር ሰሜናዊ ጫፍ በስተ ምሥራቅ 28 ኪሎ ሜትር ያህል ይርቃል፤ ኤር 48፥34 ይመ፡፡ በእስራኤል ከመያዙ በፊት የንጉሥ ሴዎን ዋና ከተማ ነበር (ዘኍ 21፥23-26 ይመ)፡፡ *ኤልያሊ፤* ከሐሴቦን አንድ ኪሎ ሜትር ተኩል ያህል የሚርቅና አብዛኛውን ጊዜ ከሐሴቦን ጋር አብሮ የሚጠራ ስፍራ ነው፡፡ *ያሀድ፤* ከአርኖን ወንዝ በስተ ሰሜን የሚገኝ ሲሆን፣ ከሐሴቦን 32 ኪሎ ሜትር ያህል ይርቃል (ዘኍ 21፥23፤ ኤር 48፥34)፡፡

15፥5 *ዞዓር፤* በስተ ደቡብ ከሙት ባሕር አጠገብ የሚገኝ ስፍራ ነው፡፡ ሎጥ ከሰዶም የሸሸው ወደዚህ ስፍራ ነበር (ዘፍ 14፥2፤ 19፥23፡30 ይመ)፡፡ *ዔግላት ሺሊሺያ፤* ቦታው የት እንደ ሆነ አይታወቅም (ኤር 48፥34 ይመ)፤ የስሙ ትርጕም ግን፣ "የሦስት ዓመት ወይፈን" ማለት ነው (ከ1ሳሙ 1፥24 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡ *ሉሒት፤* ቦታው የት እንደ ሆነ አይታወቅም (ኤር 48፥5 ይመ)፡፡ *ሖሮናይም፤* ቦታው የት እንደ ሆነ አይታወቅም (ኤር 48፥3፡5፡34 ይመ)፡፡

15፥6 *የኔምሬ ውሆች፤* ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ 16 ኪሎ ሜትር ያህል ርቆ ከሚገኘው ኢን ኑሜሪያ ከሚባለው ደረቅ ወንዝ ጋር አንድ ሊሆን ይችላል (ከ48፥34 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡ *ሣሩ ጠውልጓል፤* እየተመመ የመጣው ወራሪ ኀይል፣ ዋና ዋናዎቹን የሞዓብ ምንጮች ሳይደፍን አልቀረም፡፡

15፥7 *ከአኻያ ወንዝ ማዶ፤* ምናልባት በሞዓብና በኤዶም መካከል ባለው ድንበር ላይ የሚገኝ ይሆናል (ቍ 8 ይመ)፡፡

15፥8 *ኤግላይም፤* ምናልባት በሰሜን ሞዓብ ድንበር ላይ የሚገኝ ይሆናል፡፡ *ብኤርኢሊም፤* ብኤር ማለት፣ "የውሃ ጕድጓድ" (ከዘኍ 21፥16 ጋር ያነጻጽሩ) ማለት ሲሆን ይህ ቦታ ለደቡባዊው ድንበር ቅርብ ሳይሆን አይቀርም፡፡

15፥9 *የዲሞን ወንዞች በደም፤* "ደም" ለሚለው የሚገባው የዕብራይጥ ቃል፣ "ዲሞን" ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ ድምፅት አለው፤ ይህም በአርኖን ወንዝ አጠገብ ካለው፣ "ዲቦን" ከተባለው ጋር የሚመሳሰል ነው፡፡ በዚህ ዐይነቱ ግጭት ብዙ ሞዓባውያን ያልቃሉ፡፡ *አንበሳ፤* ቃሉ የአሦርን ሰራዊት (ከ5፥29 ጋር ያነጻጽሩ ፤ ኤር 50፥17 ይመ) አሊያም እውነተኛ አንበሶችን (ከ13፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ) ሊያመለክት ይችላል፡፡

16፥1 *ሴላ፤* ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ የምትገኝ አጠገቧ ካለችው ስፔትራ (ከ42፥11 ጋር ያነጻጽሩ) 1000 ጫማ ከፍ ብላ ቋጥኝ ባለበት ስፍራ ላይ የተመሠረተች፣ በተፈጥሮ አቀማመጧ ምሽግ የሆነች የኤዶማውያን ዋና ከተማ ናት፡፡ የስሟ ትርጕም፣ "ረዥምና ጠባብ የድንጋይ ገደል" ማለት ነው፤ ስለዚህ ግብሩ ወደ ደቡባዊ ሙት ባሕር አካባቢ ይላካል ማለት ነው፡፡ *ጽዮን ሴት ልጅ፤* ለኢየሩሳሌምና ለነዋሪዎቿ የተሰጠ ስም ነው፡፡ *የበግ ጠቦት ግብር ላኩ፤* ንጉሥ ሞሳ ለእስራኤል ንጉሥ ለአክዓብ በየዓመቱ አንድ መቶ ሺህ የበግ ጠቦት ይልክ እንደ ነበር (2ነገ 3፥4) ሁሉ አሁንም ትዕቢተኛዋ እስራኤልን ብዙ ጊዜ ታስጨንቅ የነበረችው ሞዓብ በዚህ በጭንቅ ውስጥ ባለችበት ጊዜ ኢየሩሳሌም ላለው ንጉሥ ራሷን እንድታስገዛ ተመክራለች፡፡

16፥2 *በአርኖን ወንዝ መሻገሪያ፤* ከሰሜን አቅጣጫ ከመጣው ወራሪ ኀይል ለማምለጥ፣ ሴቶች ወደ ደቡብ ይሸሹ ነበር፡፡

16፥3 *የሸሹትን ደብቁ፤* ሞዓባውያን ይሁዳን መደበቂያ ይጠይቁ ነበር (ከሩት 1፥1፤ 1ሳሙ 22፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡

[4]የሞዓባውያን ስደተኞች ከእናንተ ጋር ይቈዩ፤
እናንተም ከአጥፊው መጠጊያ ሁኗቸው።"
የጨቋኙ ፍጻሜ ይመጣል፤
ጥፋቱ ያከትማል፤
አብሪተኛም ከምድር ገጽ ይጠፋል።
[5]ዙፋን በፍቅር ይመሠረታል፤
ከዳዊት ቤት[*] የሆነ፣
በፍርድ ፍትሕን የሚሻ፣
ጽድቅንም የሚያፋጥን፣
አንድ ሰው በታማኝነት በላዩ ይቀመጣል።
[6]የሞዓብን መዘባነን፣
እጅግ መታበዩንና ኵራቱን፣
እብሪቱንና ስድነቱን ሰምተናል፤
ትምክህቱ ግን ከንቱ ነው።
[7]ስለዚህ ሞዓባውያን ዋይ ይላሉ፤
በአንድነትም ስለ ሞዓብ ዋይታ ያሰማሉ፤
ስለ ቂርሐራሴት ከተማ ሰዎች ትዝታ፣
በሐዘን ያለቅሳሉ።
[8]የሐሴቦን ዕርሻ፣
የሴባማም የወይን ተክል ጠውልጎአል፤
የአሕዛብ ገዦች፣
ኢያዜርን ዐልፈው፣
ምድረ በዳውን ዘልቀው፣
ሥሮቻቸውን
እስከ ባሕር ሰድደው የነበሩትን
የተመረጡ የወይን ተክሎችን ረጋግጠዋል።
[9]ስለዚህ ስለ ሴባማ የወይን ተክል፣
ኢያዜር እንዳለቀሰች፣ እኔም አለቅሳለሁ፤
ሐሴቦን ሆይ፤ ኤልያሊ ሆይ፤
በእንባዬ አርስሻለሁ፤
ፍሬ ባፈራሽበት ወቅት የነበረው ሆታ፣
መከርሽም ሲደርስ የነበረው ደስታ
ተቋርጦአልና።
[10]ደስታና ሐሤትም ከአትክልቱ ቦታ ተወግ
ዷል፤
በወይን ተክልም ቦታ ዝማሬ የለም፤ እልልታም
ቀርቶአል፤
በወይን መጭመቂያ ቦታ የሚረግጥ የለም፤
የረጋጮችን ሆታ አጥፍቻለሁና።
[11]ስለዚህ ልቤ ስለ ሞዓብ እንደ በገና
የሐዘን እንጒርጒሮ ታሰማለች፤
አንጀቴም ስለ ቂርሔሬስ ታለቅሳለች፤
[12]ሞዓብ ወደ ኰረብታዋ ብትወጣ፣
ትርፏ ድካም ብቻ ነው፤
ለጸሎት ወደ መቅደሷ ብትገባም፣
ዋጋ የለውም።

[13]*እግዚአብሔር* አስቀድሞ ስለ ሞዓብ የተናገ
ረው ቃል ይህ ነው። [14]አሁን ግን *እግዚአብሔር*
እንዲህ ይላል፤ "የተቀጠረ ሠራተኛ ቀን እንደ
ሚቈጥር፣ የሞዓብ ክብርና የሕዝቧ ብዛት በሦ
ስት ዓመት ውስጥ ይዋረዳል፤ የሚቀረውም ሕዝብ
ጥቂትና ደካማ ይሆናል።"

## በደማስቆ ላይ የተነገረ ንግር

**17** ስለ ደማስቆ የተነገረ ንግር፤
"እነሆ፤ ደማስቆ ከእንግዲህ ከተ
ማነቷ ይቀራል፤
የፍርስራሽ ክምር ትሆናለች።
[2]የአሮኤር ከተሞች ባድማ ይሆናሉ፤
የመንጎች መሰማሪያ ይሆናሉ፤
የሚያስፈራቸውም የለም።
[3]የተመሸገ ከተማ ከኤፍሬም፣
የመንግሥት ሥልጣን ከደማስቆ ይወርዳል፤
የሶርያም ቅሬታ
እንደ እስራኤላውያን ክብር ይሆናል"
ይላል የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር*።
[4]"በዚያን ቀን የያዕቆብ ክብር ይደበዝዛል፤
የሰውነቱም ውፍረት ይሟሽሻል።
[5]አጫጅ የቆመውን ሰብል ሰብስቦ፣
ዛላውንም በክንዱ እንደሚያጭድ፣
ይህም በራፋይም ሸለቆ
እንደሚለቀም ቃርሚያ ይሆናል።
[6]ሆኖም የወይራ ዛፍ ሲመታ፣

16፥4 ኢሳ2፥2-4፤ 9፥4፤58፥7
16፥5 1ሳሙ13፥14፤ ምሳ20፥28፤ኢሳ7፥2፤ 9፥7፤ዳን7፥14፤ ሚክ4፥7፤ሉቃ1፥32
16፥6 ዘሌ26፥19፤ ኢዮ20፥6፤ኤር25፥21፤ 49፥16፤ሕዝ25፥8፤ አሞ2፥1፤አብ1፥3፤ ሶፎ2፥8:10
16፥7 2ነገ3፥25፤ 1ዜና16፥3፤ኢሳ13፥6፤ ኤር48፥20፤49፥3
16፥8 ዘኍ21፥25: 32፤32፥3፤ኢዮ8፥16፤ መዝ80፥11፤ኢሳ5፥2፤ 15፥6
16፥9 ዘኍ32፥3፤ ኢዮ7፥3፤ዕዝ3፥13፤ ኢሳ15፥3፤ኤር40፥12፤ ሕዝ27፥31
16፥10 መሳ9፥27፤ ኢዮ24፥11፤ኢሳ5፥2፤ 24፥7-8፤ኤር25፥30
16፥11 ኢዮ30፥31፤ ኢሳ15፥5፤63፥15፤ ሆሴ11፥8፤ፊል2፥1
16፥12 1ነገ11፥7፤ 18፥29፤መዝ11፥54-7፤ ኢሳ15፥2፤44፥17-18፤ 1ቆሮ8፥4
16፥14 ዘሌ19፥13፤ 25፥50፤ኢሳ203፤ 21፥17፤25፥10፤ 37፥30፤ኤር48፥42
17፥1 ዘፍ14፥15፤ ዘዳ13፥16፤ኢሳ13፥1፤ 25፥2፤ሐሥ9፥2
17፥2 ዘሌ26፥6፤ 2ነገ10፥33፤ኢሳ5፥17፤ 7፥21፤27፥10፤ ኤር7፥33፤ሕዝ25፥5፤ ሚክ4፥4
17፥3 ቍ4፤ ኢሳ7፥8:16፤8፥4፤ 21፥16፤25፥2:12፤ ሆሴ9፥11፤10፥14
17፥4 ቍ3፤ ኢሳ2፥11፤10፥16
17፥5 ቍ11፤ ኢሱ17፥15፤ 1ዜና11፥15፤ኢዮ24፥24፤ኢሳ33፥4፤ ኤር51፥33፤ኢል3፥13፤ ማቴ13፥30
17፥6 ቍ11፤ዘዳ4፥27፤ኢሳ10፥19፤24፥13፤ 27፥12

[*]5 ዕብራይስጡ ድንኳን ይላል።

16፥4 *ከአጥፊው፤* ምናልባት አሦርን ማለት ነው (የ15፥1፤ 33፥1 ማብ ይመ)። *የጨቋኙ፤* ሞዓብ ነው።

*16፥9-11፤* ትዕቢተኛዋን ሞዓብን ለማዋረድ ወደፊት ስለሚያመጣው ጥፋት ራሱ እግዚአብሔር ያዝንላታል፤ ያለቅስላታልም።

16፥9 *ኤልያሊ፤* የ15፥4 ማብ ይመ።

16፥10 *በወይን መጭመቂያ ቦታ የሚረግጥ የለም፤* የወይኑ ፍሬ ይረገጣል፤ ከዚያም ፈሳሹ ወደ ወይን ማጠራቀሚያው ገንዳ ይወርዳል (የ5፥2 ማብ ይመ፤ ከኤር 48፥33፤ አሞ 9፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

*16፥11፤* ከኤር 48፥36 ጋር ያነጻጽሩ።

16፥12 *ኰረብታዋ፤* 15፥2እና ማብ ይመ። *ለጸሎት ወደ መቅደሷ ብትገባም፣ ዋጋ የለውም፤* የሞዓብ አምላክ ካሞሽ የሰው እጅ የሠራው ምስል ነው፤ ምንም ሊያደርግ አይችልም (44፥17-20፤ 1ነገ 11፥7 ይመ)።

*16፥13-14፤* ከ15፥1-16፥12 ባለው ላይ የተጨመረ ነው።

16፥14 *በሦስት ዓመት ውስጥ፤* ሦስት ዓመት የጊዜ ገደብ የተሰጣቸው ሌሎች ምልክቶች በ20፥3፤ 37፥30 ተጠቅሰዋል፤ የ7፥14:16 ማብ ይመ። ለሞዓብ የተሰጠው ሦስት ዓመት ከ715 ዓ.ቅ.ክ በፊት ዐልፎ ነበር (የ15፥1 ማብ ይመ)፤ *የተቀጠረ ሠራተኛ ቀን እንደሚቈጥር፤* በቁጻር ላይ የሚፈጸመው ትንቢት ከተገለጸበት ጥቅስ ከ21፥16-17 ጋር ያነጻጽሩ።

*17፥1-14፤* ኤር 49፥23-27፤ አሞ 1፥3-5 ይመ።

17፥1 *ንግር፤* የ13፥1 ማብ ይመ። *ደማስቆ፤* ከአርሞንኤም ተራራ በስተ ምሥራቅ የምትገኝ ስትሆን፣ መስጴጦምያን፣ ግብፅንና ዐረቢያን በሚያገናኝ፣ በዋናው የንግድ መስመር ላይ የተመሠረተች የሶርያ ዋና ከተማ ናት። ከዳዊት ዘመን ጀምሮ የደማስቆ አራማውያን (ሶርያውያን) ምን ጊዜም ያልተኙላቸው የእስራኤላውያን ጠላቶች ነበሩ (2ሳሙ 8፥5፤ 1ነገ 22፥31 ይመ)።

*17፥2 አሮኤር፤* ከሙት ባሕር በስተ ምሥራቅ 22 ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ በአርኖን ወንዝ አጠገብ የምትገኝ ከተማ ናት። የሶርያን ደቡባዊ ይዞታ ታመለክታለች (2ነገ 10፥32-33 ይመ)።

17፥3 *ከኤፍሬም፤* የሰሜኑ መንግሥት አሦርን ለመውጋት (የ7፥2 ማብ ይመ) ከደማስቆ ጋር ስለ ተባበረ እዚህ ቦታ ላይ ተጠቅሶአል (የ7፥1 ማብ ይመ)። *የመንግሥት ሥልጣን፤* በ732 ዓ.ቅ.ክ ቴልጌልቴልፌልሶር ሣልሳዊ ደማስቆን ይዞ የአሦር ክፍለ ሀገር አደረጋት፤ ብዙዎች የእስራኤል ከተሞችም በዚሁ ወቅት ተይዘዋል (የ9፥1 ማብ ይመ)።

*17፥4-11፤* ነቢዩ ከደማስቆ ወደ እስራኤል ዘወር ብሎአል፤ ለዚህም ዝግጅት የተደረገው በቍጥር 3 መጨረሻ ላይ ነው። ፍርዱ በደማስቆና በእስራኤል ላይ መነገሩ በምዕራፍ 7 ላይ ያለውን ተመሳሳይ ግንኙነት ያንጸባርቃል።

17፥4:7:9 *በዚያን ቀን፤* የ2፥11:17:20፤ 10፥20:27 ማብ ይመ።

17፥5 *ሰብል…በክንዱ እንደሚያጭድ፤* የሰብል መታጨድ የፍርድን ወቅት ያመለክታል (ኢል 3፥13 ይመ)። *በራፋይም ሸለቆ፤*

ሁለት ወይም ሦስት ፍሬ በቅርንጫፍ ራስ
ላይ እንደሚቀር፣
አራት ወይም አምስት ፍሬም ችፍግ
ባለው ቅርንጫፍ ላይ እንደሚቀር፣
እንዲሁ ጥቂት ቃርሚያ ይተርፋል”
ይላል የእስራኤል ስ<sup>ም</sup>ባክ
እግዚአብሔር።

[7]በዚያ ቀን ሰዎች ወደ ፈጣሪያቸው ይመለከታሉ፤
ዐይኖቻቸውም ወደ እስራኤል ቅዱስ ያያሉ።
[8]በእጆቻቸውም ወደ ሠሯቸው መሠዊያዎች
አይመለከቱም፤
በጣቶቻቸው ላበጇቸው የዕጣን
መሠዊያዎች፣
ለአሼራም የአምልኮ ዐምዶች
ክብር አይሰጡም።

[9]በዚያን ቀን በእስራኤል ልጆች ምክንያት የተተውት ጠንካራ ከተሞች ጥሻና ውድማ እንደ ሆኑ ሁሉ፣ እነዚህ ሁሉ ባድማ ይሆናሉ።

[10]አዳኝ ስ<sup>ም</sup>ባክህን ረስተሃል፤
መሸሸጊያ ዐለትህንም አላስታወስህም፤
ስለዚህ ምርጥ ተክል ብትተክልም፣
እንግዳ ዘርንም ብትዘራ፣
[11]በተከልህበት ቀን እንዲበቅል፣
በዘራህበትም ማግሥት እንዲያብብ ብታደርግ
እንኳ፣
መከሩ በደዌና በማይሽር ሕመም ቀን፣
እንዳልነበረ ይሆናል።

[12]አቤት፤ የብዙ ሕዝቦች የቍጣ ድምፅ
እንደ ባሕር ሞገድ ይጮኻል፤
አቤት፤ የሰዎች ከፍተኛ ጩኸት!
እንደ ኀይለኛ ውሃ ያስገመግማል።
[13]ሰዎቹ እንደ ኀይለኛ ውሃ ጩኸት
ቢያስገመግሙም፣
እርሱ ሲገሥጻቸው፣
በኰረብታ ላይ በነፋስ እንደሚበን ትቢያ፣
በዐውሎ ነፋስ ፊት እንደሚበተን ገለባ
ይበተናሉ።
[14]እነሆ፤ ሲመሽ ድንገተኛ ሽብር ሆነ!
ከመንጋቱ በፊት ግን አንዳቸውም
አልተገኙም።
የዘረፉን ዕድል ፈንታ፣
የበዘበዙን ዕጣ ይህ ሆነ።

## በኢትዮጵያ ላይ የተነገረ ትንቢት

**18** በኢትዮጵያ ወንዞች ዳር ለምትገኝ፣
ፉር ፉር የሚሉ ክንፎች ላሉባት[ሠ]
ምድር ወዮላት!
[2]ይህችውም መልእክተኞችን በባሕር፣
ከወንዞች ማዶ በደንገል ጀልባ የምትልክ ናት።
እናንት ፈጣን መልእክተኞች፤
ረጃጅምና ቈዳው ወደ ለሰለሰ፣
ከቅርብም ከሩቅም ወደሚፈራ ሕዝብ፣
ኀያልና ቋንቋው ወደማይገባ፣
ወንዞች ምድሩን ወደሚከፍሉት መንግሥት፣
ሂዱ!

[3]እናንት የዓለም ሕዝቦች፣
በምድርም የምትኖሩ ሁሉ፣
በተራሮች ላይ ምልክት ሲሰቀል ታዩታላችሁ፤
መለከትም ሲነፋ ትሰሙታላችሁ።
[4]እግዚአብሔር እንዲህ ብሎኛል፤
“ጸጥ ብዬ እቀመጣለሁ፤
ከማደሪያዬም በፀሓይ ሐሩር እንደሚያብረቀርቅ
ትኵሳት፣
በመከርም ሙቀት እንደ ደመና ጠል ሆኜ
እመለከታለሁ።”
[5]ከመከር በፊት የአበባው ወቅት ሲያልፍ፣
አበባው የጐመራ የወይን ፍሬ ሲሆን፣
የወይን ሐረጉን ተቀጥላ በመግረዣ ይገርዘዋል፤
የተንሰራፋውንም ቅርንጫፍ ቈራርጦ
ያስወግደዋልና።
[6]ሁሉም በተራራ ላይ ለሚኖሩ ነጣቂ አሞሮች
ለዱርም አራዊት ይተዋሉ፤
አሞሮች በጋውን ሁሉ ሲበሉት ይከርማሉ፤

17፥7 መዝ95፥6፤ ኢሳ2፥11፤9፥13፤ 10፥20፤12፥6
17፥8 ዘሌ26፥30፤ መሳ3፥7፤2ነገ17፥10፤ 2ዜና32፥19፤ኢሳ2፥8፡18፡20፤30፥22፤46፥6፤ ራእ9፥20
17፥9 ኢሳ7፥19
17፥10 ዘፍ49፥24፤ ዘዳ6፥12፤8፥11፤ መዝ18፥2፤50፥22፤ 106፥21፤ኢሳ5፥7፤ 12፥2፤51፥13፤57፥11፤ ኤር2፥32፤3፥21፤ 13፥25፤18፥15፤ ሕዝ22፥12፤23፥35፤ ሆሴ8፥14፤13፥6፤ ሉቃ1፥47
17፥11 ቍ5፤ ዘሌ26፥20፤ዘዳ28፥39፤ ኢዮ4፥8፤መዝ90፥6፤ ኤር10፥19፤30፥12፤ ሆሴ8፥7፤ኢዩ1፥11፤ ሐጌ1፥6
17፥12 ቍ13፤ መዝ18፥4፤46፥6፤ ኢሳ8፥7፡9፤41፥11፤ ሉቃ21፥25
17፥13 ዘዳ28፥20፤ ኢዮ13፥25፤21፥18፤ መዝ9፥5፤46፥3፤ 65፥7፤68፥1፤ ኢሳ2፥22፤13፥14፤ 41፥2፡15-16፤ ዳን2፥35
17፥14 2ነገ19፥35፤ ኢሳ29፥5፤30፥13፤ 33፥18፤47፥11፤48፥3፤ 54፥14
18፥1 ዘፍ10፥6፤ መዝ68፥31፤ኢሳ5፥8፤ ሕዝ29፥10
18፥2 ቍ7፤ ዘፍ10፥8-9፤41፥14፤ ዘፀ2፥3፤2ዜና12፥3፤ ኢዮ9፥26፤አብ1፥1
18፥3 ኢሳ6፥20፤ መሳ3፥27፤መዝ33፥8፤ 60፥4፤ኢሳ5፥26፤ 11፥10፤13፥2፤31፥9፤ ኤር4፥21
18፥4 መሳ5፥31፤ 2ሳሙ1፥21፤ መዝ18፥12፤ 133፥3፤ኢሳ26፥19፡21፤62፥1፤64፥12፤ ሆሴ5፥15፤14፥5፤ሚክ1፥3፤ ዕን3፥4
18፥5 ኢሳ10፥33፤ 17፥10-11፤ሕዝ17፥6
18፥6 ኢሳ8፥8፤37፥36፤56፥9፤ ኤር7፥33፤ሕዝ32፥4፤ 39፥17

[ሠ]1 ወይም፣ *አንበጣ ማለት ነው።*

ከኢየሩሳሌም በስተ ምዕራብ ያለ ለም ስፍራ ሲሆን (መሳ 15፥8)፣ ፍልስጥኤማውያን በተደጋጋሚ አደጋ ይጥሉበት ነበር (1ዜና 14፥9)።

*17፥7-8፤* ከ2፥20፤ 10፥20 *ጋር ያነጻጽሩ።*

17፥7 *እስራኤል ቅዱስ፤* የ1፥4 ማብ *ይመ።*

17፥8 *መሠዊያ፤* ምናልባት የበኣልን መሠዊያዎች የሚመለከት ነው (ከ1ነገ 16፥32 *ጋር ያነጻጽሩ*)። *ለአሼራም የአምልኮ ዐምዶች፤* የዘፀ 34፥13፤ መሳ 2፥13 ማብ *ይመ።* *የዕጣን መሠዊያዎች፤* በዘሌ 26፥30 ላይ ከተጠቀሱት ኰረብታዎችና በ2ዜና 34፥4 ላይ ከተጠቀሱት የበኣል መሠዊያዎች ጋር የተያያዘ ነው።

17፥9 *ጥሻና ውድማ፤* ከ7፥23-25 *ጋር ያነጻጽሩ።*

17፥10 *ዐለትህንም፤* 26፥4፤ 30፥29፤ 44፥8፤ ዘዳ 32፥4፡15፡18፤ መዝ 19፥14 *ይመ።* *ምርጥ ተክል፤* ምናልባት የእስራኤልን ሕዝብ የሚወክል ይሆናል (5፥7፤ 18፥5፤ 37፥30-31 *ይመ*)።

17፥11 *በደዌና በማይሽር ሕመም፤* ይህ የአሦራውያንን ወረራ ተከትሎ የመጣ ነው።

*17፥12-14፤* በ10፥28-34 ላይ በተመሳሳይ ሁኔታ ኀይለኛ ወራሪ በፍጥነት እንደሚቆም ተገልጿል። ሁለቱም ክፍሎች በ701 ዓ.ቅ.ክ የታየውን የሰናክሬምን ወረራ ያመለክታሉ። ነገር ግን ነቢዩ በዚህ ስፍራ ይበልጥ ለመግለጽ የፈለገው እስራኤልን ለማጥፋት መንግሥታት የሚያካሂዱትን ሤራ ይመስላል።

17፥12 *እንደ ባሕር ሞገድ፤* በ8፥7 ላይ አሦር፣ “ታላቅና ብርቱ የወንዝ ውሃ” ተብሎ ተጠርቶአል።

17፥13 *ትቢያ ... ገለባ፤* በምሳሌያዊ አገላለጽ ጠላትን ይገልጣል (29፥5፤ 41፥15-16፤ መዝ 83፥13 *ይመ*)።

*18፥1-7፤* ሶፎ 2፥12 *ይመ።*

18፥1 *ፉር ፉር የሚሉ ክንፎች፤* አንበጣን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል፤ ወይም በዘይቤያዊ አነጋገር የኢትዮጵያን ሰራዊት ለማመልከት የገባ ይሆናል (7፥18-19 *ይመ*)።

18፥2 *በባሕር፤* ምናልባት የዐባይን ወንዝ የሚያመለክት ይሆናል (ከ19፥5 *ጋር ያነጻጽሩ፤* ናሆ 3፥8 *ይመ*)። *በደንገል ጀልባ* የዘፀ 2፥3 ማብ *ይመ።* *ፈጣን መልእክተኞች ... ሂዱ፤* ከቍ 3-6 ያለውን መልእክት ለማድረስ ነው። *ረጃጅምና ቈዳው ወደ ለሰለሰ ሕዝብ፤* ምናልባት የኢትዮጵያንና የግብፅን ሕዝቦች የሚያመለክት ነው። ጠጕራቸውን እንደ ሴም ሕዝቦች አያሳድጉም፤ ግጥብ አድርገው ይላጩታል (የዘፍ 41፥14 ማብ *ይመ*)። *ወንዞች፤* ዐባይና ገባር ወንዞቹ።

18፥3 *እናንት የዓለም ሕዝቦች፤* በእግዚአብሔር ሕዝብ በእስራኤል ላይ የተነሡትን ሕዝቦች ሁሉ ያመለክታል (17፥12-14 እና ማብ *ይመ*)። *ምልክት፤* 5፥26 እና ማብ *ይመ።* *መለከትም፤* ዘማች ሰራዊት ለክተት የሚጠራበት መሣሪያ ነው።

18፥4 *ጸጥ ብዬ፤* መንግሥታት በጥላቻ በሚነሡበት ሰዓት እግዚአብሔር ለጊዜው ዝም ቢልም፣ እንደ በጋ ንዳድ ሆነው ሲወጡ (ቍ 5)፣ ያጠፋቸዋል።

18፥6 *አሞሮች ለዱርም አራዊት፤* ከ56፥9፤ ኤር 7፥33፤ ሕዝ

የዱር አራዊትም ክረምቱን ሁሉ ሲበሉት
ይከርማሉ።
[7]በዚያን ጊዜ ለሰራዊት ጌታ ለእግዚአብሔር፣
ረጃጅምና ቈዳው ከለሰለሰ፣
ከቅርብም ከሩቅም ከሚፈራ ሕዝብ፣
ኀያልና ቋንቋው ከማይገባ፣
ወንዞችም ምድሩን ከሚከፍሉት መንግሥት፣
ገጸ በረከት ይመጣለታል፤ ገጸ በረከቱም
የሚመጣለት የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ስም ወዳለበት ወደ ጽዮን ተራራ ነው።

## ስለ ግብፅ የተነገረ ትንቢት

**19** ስለ ግብፅ የተነገረ ንግር፤
እነሆ፤ እግዚአብሔር በፈጣን
ደመና ላይ ተቀምጦ
ወደ ግብፅ ይመጣል፤
የግብፅ ጣዖቶች በፊቱ ይርዳሉ፤
የግብፃውያንም ልብ በውስጣቸው ይቀልጣል።
[2]"ግብፃዊውን በግብፃዊው ላይ አስነሣለሁ፤
ወንድም ወንድሙን፣
ባልንጀራ ባልንጀራውን፣
ከተማም ከተማን፣
መንግሥትም መንግሥትን ይወጋል።
[3]የግብፃውያን ልብ ይሰለባል፤
ዕቅዳቸውንም መና አስቀራለሁ፤
እነርሱም ጣዖታትንና የሙታንን መናፍስት፣
መናፍስት ጠሪዎችንና ጠንቋዮችን ምክር
ይጠይቃሉ።
[4]ግብፃውያንን አሳልፌ፣
ለጨካኝ ጌታ ክንድ እሰጣቸዋለሁ፤
አስፈሪ ንጉሥም ይገዛቸዋል"
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር።
[5]የዐባይ ወንዝ ይቀንሳል፤
ውሃውም እየጐደለ ይሄዳል።
[6]መስኖዎቹ ይከረፋሉ፤
የግብፅ ጅረቶች ይጐድላሉ፤ ይጠፋሉም።
ደንገሉና ቄጠማውም ይጠወልጋል፤
[7]እንዲሁም በዐባይ ዳር፣
በወንዙ መፋሰሻ ላይ ያሉት ተክሎች
ይጠወልጋሉ።
በዐባይ ዳር የተዘራው ዕርሻ ሁሉ፣
በነፋስ ይወሰዳል፤ ምንም አይቀርም።
[8]ዓሣ አጥማጆች ያዝናሉ፤
በዐባይ ወንዝ ላይ መንጠቆአቸውን
የሚወረውሩ ሁሉ ያለቅሳሉ፤
በውሃ ላይ መረባቸውን የሚጥሉ ሁሉ፣
ጕልበታቸው ይዝላል።
[9]የተነደፈ የተልባ እግር የሚፈትሉ፣
የተባዘተ ጥጥ የሚሠሩ ሸማኔዎችም ተስፋ
ይቈርጣሉ።
[10]ልብስ ሠሪዎች ያዝናሉ፤
ደመወዝተኞችም ልባቸው ይሰበራል።

[11]የጣኔዎስ አለቆች በጣም ሞኞች ናቸው፤
የፈርዖን ጠቢባን ምክራቸው የማይረባ ነው፤
ፈርዖንን፣ "እኔ ከጥበበኞች አንዱ ነኝ፤
የጥንት ነገሥታትም ደቀ መዝሙር ነኝ"
እንዴት ትሉታላችሁ?
[12]የእናንተ ጠቢባን አሁን የት አሉ?
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
በግብፅ ላይ ያሰበውን ነገር፣
እስቲ ያሳዩአችሁ፤ ያሳውቋችሁም።
[13]የጣኔዎስ አለቆች ተሞኝተዋል፤
የሜምፊስ ሹማምንት ተታለዋል፤
የሕዝቧ ዋና ዋናዎች፣
ግብፅን አስተዋታል።
[14]እግዚአብሔር የድንዛዜን መንፈስ አፍስሶባቸዋል፤
ሰካራም በትፋቱ ዙሪያ እንደሚንገዳገድ፣
ግብፅንም በምታደርገው ነገር ሁሉ
እንድትንገዳገድ አደረጓት።
[15]ራስም ይሁን ጅራት፣ የዘንባባ ዝንጣፊም
ይሁን ደንገል፣
ለግብፅ የሚያደርጉላት አንዳች ነገር የለም።
[16]በዚያን ቀን ግብፃውያን እንደ ሴት

18፥7 ቍ 2፤ ዘፍ41፥14፤2ዜና9፥24፤ መዝ68፥31፤ኢሳ60፥7፤ ዕን1፥7
19፥1 ዘፀ12፥12፤ ዘዳ10፥14፤ኢሱ2፥11፤ 2ሳሙ22፥10፤ ኢሳ13፥1፤20፥3፤ ኤር44፥3፤ኢል3፥19፤ ራእ1፥7
19፥2 መሳ7፥22፤ 12፥4፤2ዜና15፥6፤ 20፥23፤ማቴ10፥21፤ 36፤24፥7፤ማር13፥8፤ ሉቃ21፥10
19፥3 ቍ 11፤ ዘሌ9፥31፤2ዜና10፥13፤ ኢዮ5፥12፤መዝ18፥45፤ ኢሳ47፥13፤ዳን2፥2፡10፤ 3፥8፤5፥7
19፥4 ኢሳ20፥4፤ ኤር46፥26፤ ሕዝ29፥19፤32፥11
19፥5 2ሳሙ14፥14፤ ኢሳ44፥27፤50፥2፤ ኤር50፥38፤51፥36
19፥6 ዘፍ41፥2፤ ዘፀ7፥18፤ኢዮ8፥11፤ ኢሳ15፥6፤37፥25፤ ሕዝ30፥12
19፥7 ዘኍ11፥5፤ ዘዳ29፥23፤ኢሳ23፥3፤ ዘካ10፥11
19፥8 ዘኍ11፥5፤ ሕዝ47፥10፤አሞ4፥2፤ ዕን1፥15
19፥9 ኢሱ2፥6፤ ምሳ7፥16፤ሕዝ16፥10፤ 27፥7
19፥11 ቍ 3፤ ዘፍ41፥37፤ዘኍ13፥22፤ 1ነገ4፥30፤ሐሥ7፥22
19፥12 ኢሳ14፥24፤ ሮሜ9፥17፤1ቆሮ1፥20
19፥13 ዘኍ13፥22፤ መዝ118፥22፤ ኤር2፥16፤44፥1፤ 46፥14፡19፤ሕዝ30፥13፡ 16፤ሆሴ9፥6
19፥14 መዝ107፥27፤ ምሳ12፥8፤ ማቴ17፥17
19፥15 ኢሳ9፥14 19፥16 ዘዳ2፥25፤ ኢሳ2፥17፤11፥10፡15፤ ኤር50፥37፤51፥30፤ ናሆ3፥13፤ዕብ10፥31

32፥4፤ 39፥17-20 ጋር ያነጻጽሩ።

*18፥7፤* ቍ 2 ይመ። *ገጸ በረከት፤* በ2ዜና 32፥23 መሠረት ከሰናክሬም ሞት በኋላ ለሕዝቅያስ እጅ መንሻ ይመጣለት ነበር። ሞዓባውያን ግብራቸውን ወደ ጽዮን ተራራ ማምጣት እንዳለባቸው በ16፥1 ላይ ታዝዘዋል (ከ45፥14፤ ሶፎ 3፥10 ጋር ያነጻጽሩ)። *ስም ወዳለበት፤* ዘዳ 12፥5 እና ማብ ይመ።

*19፥1-20፥6፤* ኤር 46፤ ሕዝ 29፥32 ይመ።

19፥1 *ንግር፤* የ13፥1 ማብ ይመ። *በፈጣን ደመና ላይ ተቀምጦ፤* በመዝ 68፥4፤ 104፥3 ላይ የሚገኝ ተለዋጭ ዘይቤ ነው፤ ከማቴ 26፥64 ጋር ያነጻጽሩ። *ጣዖቶች ... ይርዳሉ፤* ኤር 50፥2 ይመ። ቀደምም እግዚአብሔር ዐሥሩን መቅሠፍቶች በማውረድ በግብፅ ጣዖቶች ላይ ፈርዷል (ዘፀ 12፥12 እና ማብ ይመ)። *ልብ ... ይቀልጣል፤* 13፥7 ይመ።

19፥2 *ግብፃዊውን በግብፃዊው ላይ፤* ከ9፥21 ጋር ያነጻጽሩ። የሊብያ ሥርወ መንግሥት ከኢትዮጵያውያን (የ 18፥1 ማብ ይመ)፣ እንዲሁም ከ24ኛው ሥርወ መንግሥት ከሳይትስ ጋር ተጋጭቶ ነበር።

19፥3 *መናፍስት ጠሪዎችንና ... ምክር ይጠይቃሉ፤* እስራኤላውያንም በጭንቀታቸው ጊዜ እንዲሁ አድርገዋል (8፥19 እና ማብ ይመ)።

19፥4 *ለጨካኝ ጌታ፤* የአሦርን ንጉሥ ነው (20፥4 ይመ)። አስራዶን በ670 ዓ.ቅ.ክ ግብፅን አሸንፎ ነበር።

19፥5 *የዐባይ ወንዝ ይቀንሳል፤* የዐባይ ወንዝ ለግብፅ ሕይወቷ ነው፤ በየክረምቱ ሞልቶ በሚወርድበት ጊዜ፣ ብዙ ውሃና ደለል ስለሚዝ መሬቱን ያለማለታል።

19፥6 *መስኖዎቹም፤* የዕርሻ ቦዮች ናቸው።

19፥7 *የተዘራው ዕርሻ፤* የግብፅ ዕርሻ ምርት የተትረፈረፈ ነበር፤ ዐልፎ ተርፎም ወደ ውጭ ይላክ ነበር።

19፥8 *ዓሣ አጥማጆች፤* እጅግ ብዙ ዓሣ ይገኝ ነበር (ዘኍ 11፥5 ይመ)።

19፥9 *የተነደፈ የተልባ እግር የሚፈትሉ፤* ብዙ ተልባ ለማምረት እጅግ ብዙ ወሃ ያስፈልጋል። *የተባዘተ ጥጥ፤* ግብፃውያን ወደ ውጭ የሚልኩት ሌላው የታወቀ ምርት ነው።

19፥11 *ጣኔዎስ፤* በዐባይ መፋሰሻ ሰሜን ምሥራቅ በኩል ያለች ከተማ ናት፤ እስራኤላውያን ግብፅ በነበሩ ጊዜ ያወቋታል (ዘኍ 13፥22፤ መዝ 78፥12፡43 ይመ)። ለ25ኛው ሥርወ መንግሥት የሰሜኑ መናገሻ ከተማ ናት (የ18፥1 ማብ ይመ)። *ጠቢባን፤* ቍ 12 ይመ። ግብፅ ባሏት ብልኀ ሰዎች የታወቀች ነበረች (1ነገ 4፥30 ይመ)።

19፥13 *ሜምፊስ፤* ከዐባይ መፋሰሻ በስተ ደቡብ 24 ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ የምትገኝ በግምት ከ2686 - 2160 ዓ.ቅ.ክ የነበረው የጥንቱ መንግሥት ታዋቂ ዋና ከተማ ናት። *ዋና ዋናዎች፤* ካህናትን፣ ነቢያትንና የፖለቲካ መሪዎችን ያመለክታል (9፥15-16 ይመ)።

19፥14 *ሰካራም ... እንደሚንገዳገድ፤* ስለ እስራኤል መሪዎች መንገዳገድ በ28፥7-8 ላይ ተገልጾአል።

19፥15 *ራስም ይሁን ጅራት፣ የዘንባባ ዝንጣፊም ይሁን ደንገል፤* የግብፅን መሪዎች የሚያመለክት ነው፤ ስለ እስራኤልም መሪዎች በ9፥14-15 ላይ ተመሳሳይ አገላለጽ አለ።

*19፥16-25፤* 'በዚያን ቀን' ከሚለው ሐረግ አብሎ ጋር ተያይዘው፣

ይሆናሉ፤ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር በእነርሱ ላይ ካነሣው ክንዱ የተነሣ በፍርሀት ይንቀጠቀጣሉ። [17]የይሁዳ ምድር በግብፅ ላይ ሽብር ትነዛለች፤ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር በእነርሱ ላይ ካቀደው የተነሣ፣ ስለ ይሁዳ፣ ወሬ የሰማ ሁሉ ይሸበራል።

[18]በዚያ ቀን አምስት የግብፅ ከተሞች በከነዓን ቋንቋ ይናገራሉ፤ የሰራዊት ጌታ የእግዚአብሔርም ወገን ለመሆን ቃል ኪዳን ይገባሉ፤ ከእነዚህም ከተሞች አንዲቱ የጥፋት ከተማ ተብላ ትጠራለች።

[19]በዚያ ቀን በግብፅ ምድር መካከል ለእግዚአብሔር መሠዊያ ይሠራል፤ በድንበሯም ላይ ለእግዚአብሔር ዐምድ ይቆማል። [20]ይህም በግብፅ ምድር ለሰራዊት ጌታ ለእግዚአብሔር ምልክትና ምስክር ይሆናል፤ ከሚያስጨንቋቸውም የተነሣ ወደ እግዚአብሔር ሲጮኹ፣ አዳኝና ታዳጊ ይልክላቸዋል፤ እርሱም ያድናቸዋል። [21]እግዚአብሔር ራሱን ለግብፃውያን ይገልጣል፤ እነርሱም በዚያ ቀን እግዚአብሔርን ያውቁታል፤ በመሥዋዕትና በእህል ቍርባንም ያመልኩታል። ለእግዚአብሔር ስእለት ይሳላሉ፤ የተሳሉትንም ይፈጽሙታል። [22]እግዚአብሔር ግብፅን በመቅሠፍት ይመታታል፤ መትቶም፣ ይፈውሳቸዋል። እነርሱም ወደ እግዚአብሔር ይመለሳሉ፤ እርሱም ልመናቸውን ሰምቶ ይፈውሳቸዋል።

[23]በዚያ ቀን ከግብፅ ወደ አሦር አውራ መንገድ ይዘረጋል፤ አሦራውያን ወደ ግብፅ፣ ግብፃውያንም ወደ አሦር ይሄዳሉ፤ ግብፃውያንና አሦራውያን በአንድነት ያመልካሉ። [24]በዚያ ቀን እስራኤል፣ ከግብፅና ከአሦር ጋር የምድር በረከት ለመሆን በሦስተኛነት ትቈጠራለች። [25]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔርም፣ "ሕዝቤ ግብፅ፣ የእጄ ሥራ አሦር፣ ርስቴም እስራኤል የተባረኩ ይሁኑ" ብሎ ይባርካቸዋል።

19፥17 ዘፍ35፥5፤ ኢሳ14፥24
19፥18 መዝ22፥27፤ 63፥11፤ኢሳ10፥20፤ 17፥1፤24፥12፤32፥19፤ 48፥1፤ኤር4፥2፤ 43፥13፤44፥1
19፥19 ዘፍ28፥18፤ ኢሱ22:10፤ መዝ68፥31፤ ኢሳ10፥20
19፥20 ዘፍ21፥30፤ ዘዳ28፥29፤መሳ2፥18፤ ኢሳ25፥9፤49፥24-26
19፥21 ቍ19፤ ዘፍ27፥29፤ዘኍ30፥2፤ ዘዳ23፥21፤መዝ86፥9፤ ኢሳ11፥9፤43፥10፤ 56፥7፤60፥7፤ ሚል1፥11
19፥22 ዘፀ11፥10፤ 12፥23፤ዘዳ32፥39፤ ኢሳ45፥14፤ሕዝ33፥11፤ ሆሴ6፥1፤10፥12፤ 12፥6፤14፥1፤ ኢል2፥13፤ዕብ12፥11
19፥23 ቍ16:24፤ ዘፍ27፥29፤ኢሳ2፥3፤ 11፥16፤20፥6፤27፥13፤ 66፥23፤ሚክ7፥12
19፥24 ቍ23፤ ዘፍ12፥2፤ኢሳ11፥11
19፥25 ዘፍ12፥3፤

## በግብፅና በኢትዮጵያ ላይ የተነገረ ትንቢት

**20** ዋናው የጦር አዛዥ[ⁿ1] በአሦር ንጉሥ በሳርጎን ተልኮ፣ የአዛጦንን ከተማ ወሮ በያዘበት ዓመት፣ [2]በዚያ ጊዜ እግዚአብሔር የአሞጽን ልጅ ኢሳይያስን፣ "ማቁን ከሰውነትህ፣

ዘፀ34፥9፤ መዝ87፥4፤100፥3፤ኢሳ29፥23፤43፥7፤45፥11፤60፥21፤64፥8፤ ኤር30፥22፤ሆሴ2፥23፤ኤፌ2፥10:11-14 20፥1 ኢሱ11፥22፤13፥3፤ 2ነገ18፥17 20፥2 1ሳሙ19፥24፤ 2ነገ1፥8፤ኢሳ3፥24፤13፥1፤ሕዝ4፥1-12፤ 24፥17:23፤ሚክ1፥8፤ዘካ13፥4፤ ማቴ3፥4

ⁿ1 ዋናው የጦር አዛዥ የሚለውን ዕብራይስጡ ተርታን ይለዋል

በተከታታይ አራት መግለጫዎች ተሰጥተዋል፤ (1) ግብፅ ከእግዚአብሔር መለኮታዊ ፍርድ የተነሣ "በፍርሀት ትንቀጠቀጣለች" (ቍ 6)፤ በይሁዳም ኀይል ትሸበራለች (ቍ 16-17) (2) በግብፅ ያሉ፣ "አምስት ከተሞች"፣ "በእግዚአብሔር ስም ይምላሉ" (ቍ 18)። (3) እግዚአብሔር ለግብፃውያን ካደረገው ፈውስና ድነት የተነሣ በግብፅ መሠዊያ ይቆማል፤ ግብፃውያንም ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ያቀርባሉ (ቍ 19-22)። 4) ግብፅ፣ አሦርና እስራኤል የተጣመረ የእግዚአብሔር ሕዝብ ይሆናሉ (ቍ 23-25 ይመ)። ነቢዩ ኢሳይያስ በወቅቱ ከሚታየው ሁኔታ ባሻገር ያለውን ያመለክታል። የዓለም መንግሥታት እውነተኛውን አምላክ ሳያውቁ በትዕቢት ዕቅዳቸውን ለመፈጸም ይሯሯጣሉ፤ በእግዚአብሔርም ሕዝብ ላይ እንደ ልባቸው ይሆናሉ። ነቢዩ ግን ይህን ሁሉ ዐልፎ እነዚህ መንግሥታት እግዚአብሔርን የሚያመልኩበትን ጊዜ ይመለከታል።

19፥16:18-19:23-24 *በዚያ ቀን፤* የሚወጣው የእግዚአብሔር ቀን ማለት ነው (10፥20:27 እና ማብ ይመ፤ ከ11፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ)።

19፥16 *እግዚአብሔር ... ካነሣው ክንዱ፤* 14፥26-27 እና ማብ ይመ። *በፍርሀት ይንቀጠቀጣሉ፤* እንደ ኢያሪኮ ሕዝብ ይሆናሉ ማለት ነው (ኢሱ 2፥9:11)።

19፥17 *የይሁዳ ምድር፤* ግብፃውያን ምናልባት ከሕዝቅያስ ቤተ መንግሥት ጋር ከነበራቸው ግንኙነት የተነሣ፣ ይህን ፍርድ ያመጣባቸው የይሁዳ አምላክ መሆኑን ይገነዘባሉ።

19፥18 *አምስት፤* ምናልባት፣ "ብዙ" የሚል ስሜት፣ ሳይኖረው አይቀርም። *በከነዓን ቋንቋ ይናገራሉ፤* አንድም ግብፃውያን ለእግዚአብሔር መገዛታቸውን የሚያስረዳ ምሳሌያዊ አገላለጽ (ቍ 21-22:25)፣ አሊያም በቀጥታ በግብፅ የሚኖሩትን አይሁድ የሚያመለክት ነው። ኢየሩሳሌም በ586 ዓ.ቅ.ክ ከወደቀች በኋላ ብዙ አይሁድ ወደ ግብፅ ሸሽተው ነበር (ኤር 44፥1)። *የጥፋት ከተማ፤* ምናልባት በናቡከደነፆር የተደመሰሰችውን፣ የፀሓይ አምላክ ከተማ የተባለችውን ሄልዮፖሊስን ለማመልከት ይሆናል (ኤር 43፥12-13 ይመ)። በዕብራይስጥ፣ "ጥፋት" የሚለው ቃል፣ "ፀሓይ" ከሚለው የዕብራይስጥ ቃል ጋር ይመሳሰላል።

19፥19 *መሠዊያ፤* አንዳንዶች ይህን ዓ.ቅ.ክ በሁለተኛው ምእተ ዓመት ላይ፣ አናያስ አራተኛ የተባለ የአይሁድ ሊቀ ካህናት በግብፅ ከሠራው ቤተ መቅደስ ጋር ሲያገናኙት፣ ሌሎች ደግሞ አያሌ ግብፃውያን እግዚአብሔርን ወደ ማምለክ ከመለወጣቸው ጋር ያያይዙታል።

19፥20 *ምልክትና ምስክር፤* በኢሱ 22፥26-27 ከዮርዳኖስ ማዶ ያሉ ነገዶች በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ መሠዊያ ሲሠሩ ዓላማቸው ምን ነበር? እርሱን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ። *ከሚያስጨንቋቸውም ... ያድናቸዋል፤* አባባሉ የመጽሐፈ መሳፍንት አባባል ነው (መሳ 2፥18 ይመ)። ይህ ታዳጊና አዳኝ ማን እንደ ሆነ በግልጽ አልተቀመጠም፤ ነቢዩ ይህን በሚናገርበት ጊዜ ግን፣ ከዳዊት ቤት እንደሚወለድ በተስፋ የሚጠበቀውን መሲሕ ሳያስብ አልቀረም (11፥1-10 ይመ)።

19፥21 *ራሱን ... ይገልጣል፤* ከዘፀ 7፥5 ጋር ያነጻጽሩ። *በመሥዋዕት ... ያመልኩታል፤* አሕዛብ ስለሚያቀርቡት መሥዋዕት በ56፥7፤ 60፥7 ይመ (ከዘካ 14፥16-19 ጋር ያነጻጽሩ)።

19፥22 *ግብፅን በመቅሠፍት ይመታታል፤* ማስጨነቅና (ቍ 20) መቅሠፍት የእግዚአብሔር ቍጣ የሚገለጥባቸው ሁለት የተለመዱ የቅጣት ዐይነቶች ናቸው። በኵሩን ያጠፋው መቅሠፍት ያስከተለውን ውጤት (ዘፀ 12፥23) ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ። *ይመለሳሉ ... ይፈውሳቸዋል፤* ከ6፥10 ጋር ያነጻጽሩ፤ ይህ አባባል በቍ 20 ላይ ከተገለጸው፣ "ታዳጊና አዳኝ" ከሚለው ሐረግ ጋር ይቀራረባል። ቀደም ብሎ በነበረው ዘመን ልቡን አደንድኖ የነበረው ፈርዖን ወደ እግዚአብሔር አልተመለሰም (ዘፀ 9፥34-35)።

19፥23 *አውራ መንገድ፤* በ11፥16 ላይ ከተገለጸው ወደ ኢየሩሳሌም ከሚወስደው አውራ መንገድ ጋር ያነጻጽሩ (ያንኑ ማብ ይመ)። ለዘመናት ግብፃውያንና አሦራውያን እርስ በርሳቸው ሲዋጉ ነበር (20፥4)፤ ወደ ፊት ግን በቃለ መሐላ ወዳጅነት መሥርተው፣ እግዚአብሔርን በአንድነት ያመልካሉ (ከ25፥3 ጋር ያነጻጽሩ)። *በአንድነት ያመልካሉ፤* በአምልኮ ውስጥ ያለው ሰላምና አንድነት በ2፥2-4 ከተገለጸው ጋር አንድ ዐይነት ነው (ያንኑ ማብ ይመ፤ የቍ 21 ማብ ይመ)።

19፥25 *ሕዝቤ ግብፅ፤* ኢሳይያስ፣ ግብጽን እንደ እግዚአብሔር ሕዝብ አድርጎ ለመጥራት የቻለው "ከእሴይ ግንድ ቍጥቋጥ ይወጣል" ከሚለው ሐረግ ጋር አብሮ የሚሄድ ሆኖ ስላገኘው ሳይሆን አይቀርም (11፥1-10 ይመ)፤ ከ45፥14፤ ኤፌ 2፥11-13 ጋር ያነጻጽሩ። *ይባርካቸዋል፤* በዘፍ 12፥3 ላይ የተጻፈው ሲፈጸም ማለት ነው።

*20፥1-6፤* 16፥13-14 ለ15፥1-16፥12 ማጠቃለያ እንደ ሆነ ሁሉ፣ ይህም ምዕራፍ የ18-19 ምዕራፎች ማጠቃለያ ነው።

20፥1 *ወሮ በያዘበት፤* ምናልባት በ711 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው። *ሳርጎን፤* ከ721-705 ዓ.ቅ.ክ ላይ የገዛው ዳግማዊ ሳርጎን ሳይሆን አይቀርም፣ በብሉይ ኪዳን ስሙ የተጠቀሰው እዚህ ቦታ ብቻ ነው። *አዛጦን፤* ከአምስቱ የፍልስጥኤም ከተሞች አንዷ ናት፤ እርሷም ከጋዛ በስተ ሰሜን ምሥራቅ 29 ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ በሚድትራኒያን ባሕር አጠገብ ትገኛለች። በ713 ዓ.ቅ.ክ በንጉሥ አዙሪ አገዛዝ ሥር በነበረችበት ጊዜ በአሦራውያን ላይ ዐምፃ ነበር። እ.ኤ.አ በ1963 ዓ.ም በአዛጦን ከተማ የአንድ የአሦራውያን ሐውልት ሦስት ስብርባሪዎች ተገኝተዋል፤ ስብርባሪዎቹም የሳርጎንን ድል ያሳያሉ፤ ስሙንም ይጠቅሳሉ።

20፥2 *ማቅ፤* በተለምዶ የሐዘንተኞች ልብስ ነው፤ ነገር ግን ነቢ

ጫማህን ከእግርህ አውልቅ" ሲል ተናገረው። እርሱም እንዲሁ አደረገ፤ ዕርቃኑንና ባዶ እግሩን ተመላለሰ።

[3]ከዚያም እግዚአብሔር እንዲህ አለ፤ "ባሪያዬ ኢሳይያስ ሦስት ዓመት በግብፅና በኢትዮጵያ ለምልክትና ለማስጠንቀቂያ ዕርቃኑንና ባዶ እግሩን እንደ ሄደ፣ [4]እንዲሁ የአሦር ንጉሥ ወጣትና ሽማግሌ የሆኑትን የተማረኩ ግብፃውያንንና የተሰደዱ ኢትዮጵያውያንን ዕርቃናቸውንና ባዶ እግራቸውን ይወስዳቸዋል፤ መቀመጫቸውን ገልቦ በመስደድም ግብፅን ያዋርዳል። [5]በኢትዮጵያ ተስፋ ያደረጉ፣ በግብፅ የተመኩ ይፈራሉ፤ ይዋረዳሉም። [6]በዚያ ቀን በዚህ ባሕር ዳርቻ የሚኖረው ሕዝብ፣ 'የተመካንባቸው፣ ከአሦር ንጉሥ ለማምለጥና ነጻ ለመውጣት የተሸሸግንባቸው ምን እንደ ደረሰባቸው ተመልከቱ! እንግዲህ እኛስ እንዴት እናመልጣለን?' ይላል።"

## በባቢሎን ላይ የተነገረ ትንቢት

# 21

በባሕሩ ዳር ባለው ምድረ በዳ ላይ የተነገረ ንግር፤

ዐውሎ ነፋስ ከደቡብ እየጠራረገ እንደሚመጣ፣
  ወራሪ ከአስፈሪ ምድር፣
  ከምድረ በዳ ይመጣል።
[2]የሚያስጨንቅ ራእይ አየሁ፤
  ከሓዲ አሳልፎ ይሰጣል፤ ዘራፊ ይዘርፋል።
ኤላም ሆይ፤ ተነሺ! ሜዶን ሆይ፤ ከበቢ!
  እርሷ ያደረሰችውን ሥቃይ ሁሉ አስቀራለሁ።
[3]ወገቤ በዚህ ሥቃይ ተሞላ፤
  በምጥ ላይ እንዳለች ሴት ጭንቅ ያዘኝ፤
በሰማሁት ነገር ተንገዳገድሁ፤
  ባየሁትም ነገር ተሸበርሁ።
[4]ልቤ ተናወጠ፤
  ፍርሀት አንቀጠቀጠኝ፤
የጓጓሁለት ውጋጋን፣
  ታላቅ ፍርሀት አሳደረብኝ።
[5]ማእዱን አሰናዱ፤
  ምንጣፉን አነጠፉ፤
በሉ፤ ጠጡም!
  እናንት ሹማምንት ተነሡ፤
  ጋሻውን በዘይት ወልውሉ!
[6]ጌታ እንዲህ አለኝ፤
  "ሂድ፤ ጠባቂ አቁም፤
  ያየውንም ይናገር፤
[7]በፈረሶች የሚሳብ፣
  ሠረገሎችን ሲያይ፣
በአህያ ላይ የሚቀመጡትን፣
  በግመል የሚጋልቡትን ሲመለከት፣
ያስተውል፣
  በጥንቃቄም ያስተውል።"
[8]ጠባቂው ጮኸ፤[m] እንዲህም አለ፤
  "ጌታ ሆይ፤ በየቀኑ ማማ ላይ ቆሜአለሁ፤
  በየሌሊቱም በቦታዬ አለሁ።
[9]እነሆ፤ አንድ ሰው በፈረሶች በሚሳብ
  በሠረገላ መጥቶአል፤
እንዲህም ሲል መለሰ፤
  'ባቢሎን ወደቀች፣ ወደቀች!
የአማልክቷም ምስሎች ሁሉ፣
  ተሰባብረው ምድር ላይ ወደቁ።'"
[10]በዐውድማ ላይ የተወቃህ ሕዝቤ ሆይ፤
  ከሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
ከእስራኤል አምላክ፣
  የሰማሁትን እነግርሃለሁ።

20፥3 ቍ5፤ ዘፍ10፥6፤ ዘፀ3፥12፤ ዘዳ28፥46፤ ኢሳ8፥18፤16፥14፤ 19፥1፤22፥20፤37፥9፡ 30፤38፥7፤41፥8-9፤ 42፥1፤43፥3፡10፤ 49፥3፡5-7፤50፥10፤ 52፥13፤53፥11፤ ኤር7፥25፤ሐጌ2፥23፤ ዘካ4፥14
20፥4 ኢዮ12፥17፤ ኢሳ3፥24፤18፥1፤ 19፥4፤47፥3፤ ኤር13፥22፡26፤ 46፥19፤ናሆ3፥5፡10፤ ሶፎ2፥12
20፥5 ቍ3፤ 2ነገ18፥21፤ኢሳ8፥12፤ 30፥5፤ሕዝ29፥16
20፥6 2ነገ18፥21፤ ኢሳ2፥11፤10፥3፤ 19፥23፤ኤር30፥15-17፤ 31፥2፤46፥25፤ ማቴ23፥33፤1ተሰ5፥3፤ ዕብ2፥3
21፥1 ኢዮ1፥19፤ ኢሳ13፥1፡21፤ ኤር50፥12፤51፥43፤ ዳን11፥40፤ዘካ9፥14
21፥2 ዘፍ10፥22፤ መዝ60፥3፤ኢሳ13፥3፤ 22፥6፤24፥16፤33፥1፤ ኤር25፥25፤51፥28
21፥3 ዘፍ3፥16፤ ኢዮ14፥22፤መዝ48፥6፤ ኢሳ26፥17፤37፥3፤ ኤር30፥6፤48፥41፤ 49፥22፤ዳን7፥28፤ 8፥27፤10፥16፤ ዮሐ16፥21
21፥4 መዝ55፥5፤ ኢሳ7፥4፤13፥8፤35፥4፤ ዘዳ5፥9
21፥5 2ሳሙ1፥21፤ 1ነገ10፥16-17፤ ኢሳ5፥12፤22፥2፡13፤ 23፥7፤24፥8፤32፥13፤ ኤር25፥16፡27፤46፥3፤ 51፥11፡39፡57፤ ዳን5፥2
21፥6 2ነገ9፥17 21፥7 ቍ9፤መሳ6፥5 21፥8 ሚክ7፥7፤ዕን2፥1
21፥9 ቍ7፤ዘሌ26፥30፤ኢሳ2፥18፤13፥1፤46፥1፤47፥1፡5፡11፤ ኤር50፥2፤51፥8፡44፤ራእ14፥8 21፥10 ኢሳ27፥12፤28፥27፡28፤ 41፥15፤ ኤር51፥33፤ሚክ4፥13፤ዕን3፥12፤ማቴ3፥12

[m]8 የሙት ባሕር ጥቅልና የሱርስቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ አንበሳ ጮኸ ይላል።

ያትም አዘውትረው ሊለብሱት ይችላሉ (2ነገ 1፥8፤ ዘካ 13፥4 ይመ)።

20፥3 *ባሪያዬ፤* እግዚአብሔር ነቢያትንና ሌሎቹንም ለመጥራት የተጠቀመበት መጠሪያ ነው። *ሦስት ዓመት፤* 16፥14 እና ማብ ይመ። *ለምልክትና ለማስጠንቀቂያ፤* 8፥18፤ 7፥3፡14 እና ማብ ይመ። የነቢዩ የሕዝቅኤል ባሕርይ ምሳሌነቱ እጅግ ጠቃሚ ትርጒም አለው (ሕዝ 24፥24፡ 27፤ ከዘካ 3፥8 ጋር ያነጻጽሩ)። *በግብፅና በኢትዮጵያ፤* 18፥1፤ 19፥1 ይመ።

20፥4 *ዕርቃናቸውንና ባዶ እግራቸውን፤* ከ2ዜና 28፥15፤ ሚክ 1፥8 ጋር ያነጻጽሩ።

20፥5 *በኢትዮጵያ ተስፋ ያደረጉ፣ በግብፅ የተመኩ፤* አሦር በ722 - 721 ዓ.ቅ.ክ ላይ የሰሜኑን መንግሥት እስራኤልን ካሸነፈ በኋላ፣ የይሁዳ ንጉሥ ሕዝቅያስ ከግብፅ ጋር እንዲተባበር የሚያስገድድ ከባድ ግፊት ነበረበት። ኢሳይያስ ግን ይህን ዕቅድ አጥብቆ ተቃውሞታል (ከ30፥1-2፤ 31፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

21፥1 *ባሕሩ፤* ከባቢሎን በስተ ደቡብ ያለውን የፋርስ ባሕረ ሰላጤ ሊያመለክት ይችላል፤ ወይም በኤፍራጥስና በጤግሮስ ወንዞች፣ እንዲሁም በገባሮቻቸው የተከማቸው ደለል የሚፈጥረውን የአሸዋማ ሜዳ ሊሆን ይችላል። *ምድረ በዳ፤* የሚመጣው ፍርድ ባቢሎንን (ቍ 9) ምድረ በዳ ያደርጋታል (ከ13፥20-22 ጋር ያነጻጽሩ)። *ንግር፤* የ13፥1 ማብ ይመ። *ዐውሎ ነፋስ ... ከምድረ በዳ፤* ምድረ በዳ አንዳንድ ጊዜ ኀይለኛ ነፋስ እንዲነፍስ ያደርጋል (ሆሴ 13፥15 ይመ)። *ወራሪ፤* ከበረሓ ይምጣ ወይም "ከአሸባሪ ምድር" የታወቀ ነገር የለም።

21፥2 *ኤላም፤* የ11፥11 ማብ ይመ። የኤላም ሰዎች የአሦርና የባቢሎን ዋና ጠላት ነበሩ፤ ከብዙ ጊዜ በኋላም በ539 ዓ.ቅ.ክ ላይ ቂሮስ ባቢሎንን ባሸነፈ ጊዜ፣ በፋርስ ሰራዊት ውስጥ ነበሩ። *ሜዶን፤* የ13፥17 ማብ ይመ። *ያደረሰችውን፤* ባቢሎንን ነው።

21፥3 *ወገቤ ... ጭንቅ ያዘኝ፤* በዳን 8፥27፤ 10፥16-17 ላይ ዳንኤል ካየው ራእይ የተነሣ፣ ያደረበትን ስሜት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ፤ ነገር ግን የ29፥9-11 ማብ ይመ።

21፥4 *ውጋጋን፤* ምናልባትም የባቢሎንን ዐጼያዊ መንግሥት ፍጻሜ የሚያመለክት ነው (የቍ 12 ማብ ይመ)። *ታላቅ ፍርሀት አሳደረብኝ፤* የደረሰው ጥፋት ከገመተውም በላይ ነው።

21፥5 *በሉ፤ ጠጡም፤* በቤልሻጻርም ግብዣ ላይ ተመሳሳይ ሁኔታ ደርሶአል (ዳን 5፥1 ይመ)። *ተነሡ፤* ባቢሎናውያን ሲወረሩ በራእይ የተመለከተው ነቢይ በመልስ አዘል ጥያቄ የባቢሎንን መኳንንት ለውጊያ እንዲነሡ ያሳስባል። *ጋሻውን ... ወልውሉ፤* ጋሻው የተለበደበትን ቈዳ፣ ቅባት መቀባትና መወልወል የሚያርፍበትን ፍላጻ፣ ጦር ወይም ሰይፍ በቀላሉ እንዲታጠፍ ያደርጋል።

21፥6 *ሂድ፤ ጠባቂ አቁም፤* ምናልባት በኢየሩሳሌም ቅጥሮች ላይ ለማለት ይሆናል።

21፥7 *ሠረገሎችን ... በአህያ ... በግመል፤* ከሩቅ የሚመጡ መልእክተኞችን ያመለክታል።

21፥9 *ባቢሎን ወደቀች፤* 13፥19 ይመ። ባቢሎን በመጀመሪያ በ689 ዓ.ቅ.ክ እንደ ገናም በ539 ዓ.ቅ.ክ ላይ ወደቀች። እነዚህን ቃሎች ዮሐንስ በራእይ 14፥8፤ 18፥2 ጠቅሶአቸዋል። *የአማልክቷም ... ወደቁ፤* የአንድ መንግሥት መውደቅ ማለት የአማልክቷ መዋረድ ማለት ነው።

21፥10 *በዐውድማ ላይ፤* ዐውድማ በፍርድ ወይም በጦርነት መጥፋትን የሚያመለክት ተለዋጭ ዘይቤ ነው (አሞ 1፥3 ይመ)። *የተወቃህ፤* ይሁዳ በባቢሎናውያን ትቀጣለች፤ ተማርካም ትወሰዳለች (39፥5-7 ይመ)፤

## በኤዶም ላይ የተነገረ ትንቢት

[11]ስለ ኤዶም የተነገረ ንግር፤
አንዱ ከሴይር ጠርቶኝ፣
“ጠባቂ ሆይ፤ ሊነጋ ምን ያህል ቀረው?
ጠባቂ ሆይ፤ ሊነጋ ምን ያህል ቀረው?” አለኝ።
[12]ጠባቂውም መለሰ፤
“ይነጋል፤ ግን ተመልሶ ይመሻል፤
መጠየቅ ከፈለጋችሁ፣ ጠይቁ፤
ነገር ግን ተመልሳችሁ ኑ” አለ።

## በዐረብ ላይ የተነገረ ትንቢት

[13]ስለ ዐረብ አገር የተነገረ ንግር፤

እናንተ በዐረብ ዱር የምትሰፍሩ፣
የድዳን ሲራራ ነጋዴዎች፣
[14]ለተጠሙ ውሃ አምጡ።
በቴማን የምትኖሩ፣
ለስደተኞች ምግብ አምጡ።
[15]ከሰይፍ፣
ከተመዘዘ ሰይፍ፣
ከተደገነ ቀስት፣
ከተፋፋመ ጦርነት ሸሽተዋልና።

[16]ጌታም እንዲህ አለኝ፤ “በውል የተቀጠረ ሠራተኛ ቀን እንደሚቈጥር፣ የቄዳር ክብር በአንድ ዓመት ውስጥ ያበቃለታል። [17]የተረፈው ቀስተኛ፣ የቄዳር ጦረኛ ጥቂት ይሆናል፤ የእስ ራኤል አምላክ እግዚአብሔር ተናግሮአልና።”

## ስለ ኢየሩሳሌም የተነገረ ትንቢት

**22** ስለ ራእይ ሸለቆ የተነገረ ንግር፤
እስቲ ምን ቢጨንቃችሁ ነው፤
ሁላችሁም ሰገነት ላይ የወጣችሁት?
[2]አንቺ ጫጫታ የሞላብሽ ከተማ፤
የውካታና የፈንጠዝያ ከተማ ሆይ፤
የተገደሉብሽ በሰይፍ የተሠዉ አይደሉም፤
በጦርነትም አልሞቱም።
[3]መሪዎችሽ በሙሉ በአንድ ላይ ሸሽተዋል፤
ቀስት እንኳ ሳያነሡ ተማርከዋል፤
ጠላት ገና በሩቅ ሳለ የሸሻችሁ ሁሉ፣
ተይዛችሁ በአንድነት ታስራችኋል።
[4]ስለዚህ፣ “ከእኔ ራቁ፤
አምርሬ ላልቅስበት፣
ስለ ሕዝቤ ጥፋት፣
ልታጽናኑኝ አትሞክሩ” አልሁ።

[5]እግዚአብሔር የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
በራእይ ሸለቆ፣
የመጯጯኺያ የመረገጥና የሽብር፣
ቅጥሮችን የማፈራረስ፣
ወደ ተራሮችም የሚጮኹበት ቀን አለው።
[6]ኤላም የፍላጻ ሰገባ፣
ፈረሷንና ሠረገላዋን አዘጋጀች፤
ቂርም ጋሻዋን አነገበች
[7]መልካሞቹ ሸለቆዎችሽ በሠረገሎች
ተሞልተዋል፤
ፈረሰኞችም በከተማዪቱ በሮች ላይ ቆመዋል፤
[8]የይሁዳን መከላከያዎች ገልጧል።

በዚያን ቀን በዱር ግምጃ ቤት የነበረውን፣
የጦር መሣሪያ ተመለከትህ፤
[9]የዳዊት ከተማ፣
ብዙ ፍርስራሾች እንዳሉበት አያችሁ፤
በታችኛውም ኵሬ፣
ውሃ አጠራቀማችሁ።

21፥11 ዘፍ25፥14፤ 32፥3፤ኢሳ34፥11
21፥13 ዘፍ10፥7፤ 25፥3፤2ዜና9፥14፤ ኢሳ13፥1
21፥14 ዘፍ25፥15
21፥15 ኢሳ13፥14፤ 31፥8
21፥16 ዘፍ25፥13፤ ዘሌ25፥50፤ኢሳ17፥3
21፥17 ዘዳ4፥27፤ ኢሳ1፥20፤10፥19፤ 16፥14
22፥1 ኢሱ2፥8፤ መዝ125፥2፤ኢሳ1፥1፤ 13፥1፤ኤር21፥13፤ 48፥38፤ኢል3፥2፡12፡14
22፥2 2ነገ25፥3፤ ኢሳ5፥14፤10፥4፤ 21፥5፤ሕዝ22፥5
22፥3 2ነገ25፥6፤ ኢሳ13፥14
22፥4 ኢሳ15፥3፤ ኤር9፥1፤ሰቆ1፥16፤ ሕዝ21፥6፤ሉቃ19፥41
22፥5 2ሳሙ22፥43፤ ነህ6፥15፤ኢዮ40፥12፤ መዝ89፥40፤108፥13፤ ኢሳ1፥1፤2፥12፤5፥5፤ 13፥3፤ኤር30፥7፤ 39፥8፤ሰቆ1፥5፤ ሕዝ8፥17-18፤9፥9-10፤ 13፥14፤ኢል2፥31፤ አሞ5፥18-20፤ሶፎ1፥15
22፥6 2ነገ16፥9፤ መዝ46፥9፤ኢሳ21፥2፤ ኤር49፥35፤51፥56
22፥7 ኢሱ15፥8፤ 2ዜና32፥1-2
22፥8 1ነገ7፥2፤ 2ዜና32፥5፤ኢሳ2፥12
22፥9 2ነገ18፥17፤ 2ዜና32፥4፤ነህ1፥3

*21፥11-12፤* ኤር 49፥7-22፤ ሕዝ 25፥12-14፤ አሞ 1፥11-12 *ይመ*።

21፥11 ***ንግር፤*** የ13፥1 ማብ ይመ። ***ሴይር፤*** ሌላው የኤዶም ስም ነው (ዘፍ 32፥3)፤ የዔሳው ልጆች አገር ሲሆን፣ ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ ይገኛል፤ ስለ ኤዶም በ34፥5-15 ላይ በስፋት ተገልጾአል (ከ63፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

21፥12 ***ይነጋል፤ ... ይመሻል፤*** ምናልባት ጨለማው የረዘመበትን የአሦራውያንን ጭቈና ማብቃት ሲያመለክት፣ “አጭር ንጋት” ከባቢሎናውያን አገዛዝ በፊት ቀደም እንደሚል ያመለክታል።

*21፥13-17፤* ኤር 49፥28-33 ይመ።

21፥13 ***ንግር፤*** የ13፥1 ማብ ይመ። ***ዱር፤*** ነጋዴዎቹ ከወራሪዎች የሚደበቁበት ስፍራ ነው (ከመሳ 5፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። በ732 ዓ.ቅ.ክ ላይ አሦራውያን ዐረቦችን ማጥቃት ጀመሩ ባቢሎናውያንም እንዲሁ በናቡከደነፆር ስር ሳሉ ዐረቦችን ወረሩ (ኤር 25፥17፡23-24 ይመ)። ***ድዳን፤*** የዐረብ ነጋዴዎች ሲሆኑ፣ የንግድ እንቅስቃሴያቸው በሕዝ 27፥20፤ 38፥13 ተገልጾአል።

21፥14 ***በቴማን፤*** ከባቢሎን በስተ ደቡብ ምዕራብ 540 ኪሎ ሜትር ርቆ በሰሜን ዐረብ ምድረ በዳ ውስጥ የሚገኝ ውሃ ያለበት ለምለም ስፍራ ነው (ከኢዮ 6፥19፤ ኤር 25፥23 ጋር ያነጻጽሩ)።

21፥15 ***ሰይፍ ... ከተደገነ ቀስት፤*** የዐረቦች ቀስት ከአሦራውያን ሰይፍና ልዩ ቀስት ጋር እስከዚህ ሊወዳደር እንደማይችል ያመለክታል።

21፥16 ***በውል የተቀጠረ ሠራተኛ ቀን እንደሚቈጥር፤*** 16፥14 እና ማብ ይመ። ***ክብር፤*** 14፥11፤ 16፥14 ይመ። ***ቄዳር፤*** በዐረብ ምድረ በዳ የበደዊ ነገዶች የሚኖሩበት አገር ነው። ቄዳር በበግ መንጋው እጅግ ይታወቃል (60፥7፤ ሕዝ 27፥21)፤ ናቡከደነፆር የቄዳርን ሕዝብ አሸንፎአል (ኤር 49፥28-29፤ ከኤር 2፥10 ጋር ያነጻጽሩ)።

21፥17 ***የተረፈው ... ጥቂት ይሆናል፤*** ከ10፥19፤ 16፥14፤ 17፥6 ጋር ያነጻጽሩ።

*22፥1-13፤* በነዚህ ቍጥሮች ውስጥ የተጠቀሱት ማስታወሻዎች ኢየሩሳሌም በ588 - 586 ዓ.ቅ.ክ ለመጨረሻ ጊዜ በባቢሎናውያን ስትከበብ የነበረውን ትንቢት የሚያመለክቱ ናቸው። ነገር ግን በመጀመሪያ የተጠቀሰው የአሦር ንጉሥ ሰናክሬም በ701 ዓ.ቅ.ክ ላይ ኢየሩሳሌምን የያዘበትን ሁኔታ የሚያመለክት ነው።

22፥1 ***ንግር፤*** የ13፥1 ማብ ይመ። ***ራእይ ሸለቆ፤*** እግዚአብሔር ራሱን በራእይ የገለጠበት ሸለቆ ነው፤ ምናልባት በኢየሩሳሌም አካባቢ ካሉት ሸለቆዎች አንዱ ሳይሆን አይቀርም (የቍ 7 ማብ ይመ)፤ ቍ 5 ይመ። ***ሰገነት፤*** 15፥3 ማብ ይመ።

22፥2 ***የውካታና የፈንጠዝያ፤*** ቍ 13፤ 5፥11-12፤ 32፥13 ይመ። ኢየሩሳሌም የባቢሎንን ባሕርይ መከተል ጀምራ ነበር (21፥5 ይመ፤ ከ23፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። ***የተገደሉብሽ በሰይፍ ... አይደሉም፤*** ባቢሎናውያን በ586 ዓ.ቅ.ክ ላይ ኢየሩሳሌምን በከበቡ ጊዜ በራብና በበሽታ ያለቁትን ሰዎች የሚያመለክት ነው።

22፥3 ***መሪዎችሽ ... ሸሽተዋል፤*** ንጉሥ ሴዴቅያስና ጦር ሰራዊቱ ከኢየሩሳሌም ሸሽተዋል፤ ይሁን እንጂ አላመለጡም፤ ኢያሪኮ አጠገብ ተይዘዋል (2ነገ 25፥4-6 ይመ)።

22፥5 ***ቀን አለው፤*** 2፥12 እና የ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ። ***የመጯጯኺያ፤*** የዘዳ 28፥20 ርግማን መፈጸሙን ያመለክታል።

22፥6 ***ኤላም፤*** የ11፥11 ማብ ይመ። የኤላም ሰዎች ምናልባት በባቢሎን ጦርነት ሳይሳተፉ አልቀሩም። ***ቂር፤*** ሌላው የሜዶን ስም ሳይሆን አይቀርም (21፥2 ይመ)።

22፥7 ***መልካሞቹ ሸለቆዎችሽ፤*** የቄድሮን ሸለቆ ከኢየሩሳሌም በስተ ምሥራቅ (ዮሐ 18፥1 ይመ)፣ የሄኖም ደግሞ በደቡብና በምዕራብ ኢየሩሳሌም ይገኛሉ (ኢሱ 15፥8 ይመ)።

22፥8 ***በዱር ግምጃ ቤት፤*** ንጉሥ ሰሎሞን ከሊባኖስ በመጡ ዝግባዎች ያሠራው ሳይሆን አይቀርም (1ነገ 7፥2-6፤ 10፥17፡21 ይመ)።

22፥9 ***የዳዊት ከተማ፤*** 2ሳሙ 5፥6-7፡9 ይመ። ***በታችኛውም ኵሬ፤*** በቍ 11 “የጥንቱ ኵሬ” ከተባለው ጋር ተመሳሳይ ሳይሆን አይቀርም። ንጉሥ ሕዝቅያስ የሰናክሬም ወረራ የሚያስከትለውን ችግር አስቀድሞ በመረዳት የውሃ ኵሬና እንደ ዛሬው ዘመን የውሃ መስመር (ቧምቧ የሚያገለግል ትልቅ የመሬት ውስጥ ለውስጥ ቦይ

10በኢየሩሳሌም ያሉትን ቤቶች ቈጠራችሁ፤
  ቅጥሩን ለመጠገንም ቤቶቹን አፈረሳችሁ።
11ለጥንቱ ኵሬ ውሃ የሚሆን፣
  በሁለቱ ቅጥሮች መካከል ውሃ ማጠራቀሚያ
    ሠራችሁ፤
ነገር ግን ይህን ያደረገውን አልተመለከ
    ታችሁም፤
  ቀድሞ ዐቅዶ የሠራውንም አላስታወሳችሁም።

12በዚያን ቀን ጌታ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
  እንድታለቅሱና በዋይታ እንድትጮኹ፣
ጠጕራችሁን እንድትነጩ
  ማቅም እንድትለብሱ ጠራችሁ።
13ነገር ግን እነሆ፤ ተድላና ደስታ፣
  ፍሪዳ መጣልና ሙክት ማረድ፣
ሥጋ መብላትና የወይን ጠጅ መጠጣት አለ፤
  "እንብላ እንጠጣ
  ነገ እንሞታለንና" አላችሁ።

14የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ይህን ገለጠ ልኝ፤ እንዲህም ሲል በጆሮዬ ሰማሁ፤ "ይህ ኀጢአት እስከምትሞቱበት ቀን ድረስ አይ ሰረይላችሁም" ይላል ጌታ የሰራዊት ጌታ እግዚ አብሔር።

15ጌታ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ
    ይላል፤

  "ሂድና ይህን መጋቢ፣
  የቤቱንም ኀላፊ ሳምናስን እንዲህ በለው፤
16'እዚህ ምን ታደርጋለህ?
  በዚህ ስፍራ ለራስህ መቃብርን እንድታዘጋጅ፣
በከፍታውም ላይ መቀበሪያህን እንድትወቅር፣
  ራስህ የሚያርፍበትንም ዐለት እንድትጠርብ
    ማን ፈቀደልህ?'

17አንተ ኀያል ሰው ሆይ፤ ተጠንቀቅ፤
  እግዚአብሔር አጥብቆ ሊይዝህ፣ በእጆቹም
    ጨብጦ ሊወረውርህ ነው።
18አዙሮ አዙሮ እንደ ኳስ አጡዞ፣
  ወደ ሰፊ አገር ይወነጭፍሃል፤
አንተ የጌታህ ቤት ዕፍረት!
  በዚያ ትሞታለህ፤
  የክብር ሠረገሎችህም እዚያ ይቀራሉ።
19ከማዕረግህ አወርድሃለሁ፤
  ከኀላፊነትህም ትባረራለህ።

20"በዚያን ቀን አገልጋዬን፣ የኬልቅያስን ልጅ ኤልያቄምን እጠራለሁ፤ 21መጐናጸፊያህን አለብሰዋለሁ፤ መታጠቂያህን አስታጥቀዋለሁ፤ ሥልጣንህንም አስረክበዋለሁ። እርሱም በኢ የሩሳሌም ለሚኖሩ፣ ለይሁዳም ቤት አባት ይሆናል። 22የዳዊትን ቤት መክፈቻ በጫንቃው ላይ አደርጋለሁ፤ እርሱ የሚከፍተውን ማንም አይዘጋም፤ የሚዘጋውንም ማንም አይከፍትም። 23በአስተማማኝ ስፍራ እንደ ካስማ እተክለዋለሁ፤ ለአባቱም ቤት የክብር ዙፋን" ይሆናል። 24የቤተ ሰቡ ክብር፣ ልጅና የልጅ ልጅ፣ እን ዲሁም ከማሰሮ ጀምሮ እስከ ጋን ድረስ ያለ የቤት ዕቃ ሁሉ በርሱ ላይ ይንጠለጠላል።

25"በዚያ ቀን" ይላል የሰራዊት ጌታ እግ ዚአብሔር፣ "በአስተማማኝ ስፍራ የተተከለ ካስማ ይነቀላል፤ ተሰብሮም ይወድቃል፤ በእር ሱም ላይ የተንጠለጠለው ሸክም ወድቆ ይከ ስከሳል፤" እግዚአብሔር ይህን ተናግሮአልና።

## ስለ ጢሮስ የተነገረ ትንቢት

**23** ስለ ጢሮስ የተነገረ ንግር፤
  የተርሴስ መርከቦች ሆይ፤ ዋይ በሉ፤
ጢሮስ ተደምስሳለችና፤
  ያለ ቤትና ያለ ወደብ ቀርታለች።

1ነገ5፥1፤10፥22፤ኢሳ2፥16፤13፥6፤ኤር47፥4፤ሕዝ26፥4፤ኢል3፥4-8፤አሞ1፥9-10፤ ዘካ9፥2-4

"23 ወይም፣ መቀመጫ ተብሎ መተርጐም ይችላል።

22፥10 2ዜና32፥5፤ ኤር33፥4
22፥11 1ሳሙ12፥24፤ 2ነገ19፥25፤25፥4፤ 2ዜና32፥4:5፤ ኤር39፥4
22፥12 ዘሌ13፥40፤ ኢሳ2፥12፤3፥24፤ ኢል1፥9፤2፥17፤ ሚክ1፥16
22፥13 1ሳሙ25፥36፤ መክ8፥15፤ኢሳ5፥22፤ 21፥5፤28፥7-8፤ 56፥12፤ሉቃ17፥26-29፤ 1ቆሮ15፥32
22፥14 1ሳሙ2፥25፤ ኢሳ5፥9፤13፥11፤ 26፥21፤30፥13-14፤ ሕዝ24፥13
22፥15 ቍ21፤ ዘፍ41፥40፤2ነገ6፥30፤ 18፥18
22፥16 ዘፍ50፥5፤ ዘኍ32፥42፤ማቴ27፥60
22፥17 ኤር10፥18፤ 13፥18፤22፥26
22፥18 ዘፍ41፥43፤ ኢዮ18፥11፤ ኢሳ14፥19፤17፥13
22፥19 1ሳሙ2፥7፤ መዝ52፥5፤ሉቃ16፥3
22፥20 ቍ25፤ 2ነገ18፥18፤ኢሳ20፥3፤ 36፥3
22፥21 ቍ15፤ ኢሳ5፥27
22፥22 1ዜና9፥27፤ ኢዮ12፥14፤ ኢሳ7፥2፤9፥6፤ ማቴ16፥19፤ራእ3፥7
22፥23 ቍ25፤ 1ሳሙ2፥7-8፤ዕዝ9፥8፤ ኢዮ6፥25፤36፥7፤ ሕዝ15፥3፤ዘካ10፥4
22፥25 ቍ20:23፤ ኢሳ46፥11፤ሚክ4፥4
23፥1 ዘፍ1፥2፤ 10፥4፤ኢሱ19፥29፤

ሠርቶ ነበር 2ነገ 20፥20 ይመ)። "ለላይኛው ኵሬ" በ7፥3፤ 36፥2 ተጠቅሶአል።

22፥10 *ቅጥሩን ለመጠገንም፤* በ2ዜና 32፥5 ላይ ሕዝቅያስ ካደረገው ዝግጅት ጋር ያነጻጽሩ።

22፥11 *ይህን ያደረገውን አልተመለከታችሁም፤* በ31፥1 ላይ ከእግዚአብሔር ይልቅ በፈረሶችና በሠረገሎች የታመኑ በተመሳሳይ ሁኔታ ተወቅሰዋል።

22፥12 *ጠጕራችሁን እንድትነጩ፤* ጠጕር ወይ ይላጫል ወይ ይነጫል (ከኤር 16፥6፤ ሕዝ 27፥31 ጋር ያነጻጽሩ)።

22፥13 *ተድላና ደስታ፤* በ35፥10፤ 51፥11 ላይ ተመሳሳይ የዕብራይስጥ ቃል ተጠቅሶአል፤ ምንባቦቹ ከምርኮ መልስ ጋር የተያያዘ ታላቅ ደስታን የሚያመለክቱ ናቸው፤ ነገር ግን ይህ ጊዜ የሐዘን ወቅት ነበር (መክ 3፥4)፤ የቍ 2 ማብ ይመ።

22፥15 *ሳምናስ፤* የሌላ አገር ሰው፣ ምናልባትም ግብፃዊ ሳይሆን አይቀርም፤ የኖረውም በሕዝቅያስ ዘመን ነበር። *የቤቱንም ኀላፊ፤* በተዋረድ ከንጉሡ ቀጥሎ ያለ ሥልጣን ነው (የቍ 21 ማብ ይመ፤ ከ36፥3፤ 1ነገ 4፥6፤ 2ነገ 15፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

22፥16 *መቃብርን እንድታዘጋጅ፤* የአንድን ሰው መቀበሪያ ስፍራ ማዘጋጀት እጅግ አስፈላጊ ነው፤ ሳምናስም ለአንድ ንጉሥ የሚገባ መቃብር ለራሱ ማሠራት ፈለገ (ከ2ዜና 16፥14 ጋር ያነጻጽሩ)።

22፥17 *ጨብጦ ሊወረውርህ፤* ከኤር 22፥24-26 ጋር ያነጻጽሩ።

22፥18 *በዚያ ትሞታለህ፤* በክብር አትቀበርም ማለት ነው (የ14፥19 ማብ ይመ)። *ሠረገሎችህም፤* የመንደላቀቅ ሕይወትና የከፍተኛ ሥልጣን ምልክት ነው (2፥7፤ ዘፍ 41፥43 ይመ)።

22፥20 *በዚያን ቀን፤* እግዚአብሔር በሚፈርድበት ቀን ማለት ነው (ቍ 17-19 ይመ)። *አገልጋዬን፤* የ20፥3 ማብ ይመ። ኤልያቄምን፤ 36፥3፡11፡22፤ 37፥2 ይመ።

22፥21 *ሥልጣንህን አስረክበዋለሁ፤* በ701 ዓ.ቅ.ክ ላይ (36፥3 ይመ) ኤልያቄም ሳምናስን ተካው፤ ሳምናስም ወደ ጸሓፊነት ደረጃ ወረደ።

*22፥22፤* በራእ 3፥7 ላይ በከፊል ተጠቅሶአል። በቍ 21 ላይ "አባት" እና ስለ ኀላፊነቱም፣ "በጫንቃው ላይ አደርጋለሁ" የሚለው መጠቀሱ ስለ መሲሑ በ9፥6 ላይ የተጠቀሰውን ያስታውሰናል። *የዳዊትን ቤት መክፈቻ፤* ከዳዊት ቤት ለሚወለደው ከንጉሡ የተሰጠውን የሥልጣን ውክልና የሚያመለክት ነው፤ ምናልባት ወደ ቤተ መንግሥቱ የሚያስገባውን በር የሚቈጣጠርበት ሥልጣን ይሆናል። በማቴ 16፥19 ላይ ለጴጥሮስ ከተሰጠው ሥልጣን ጋር ያነጻጽሩ።

22፥23 *ካስማ፤* የዕብራይስጡ ቃል የድንኳንን ካስማ የሚያመለክት ቢሆንም፣ በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው በቤት ውስጥ ተመቶ የሚገባውን ነው (ሕዝ 15፥3 ይመ)። *የክብር ዙፋን፤* ከ1ሳሙ 2፥8 ጋር ያነጻጽሩ።

22፥25 *በዚያ ቀን፤* መቼ እንደ ሆነ በውል ተለይቶ ያልታወቀ እግዚአብሔር የሚፈርድበት ቀን ነው። *ካስማ ይነቀላል፤* ኤልያቄምም ሳይታሰብ እንደ ሳምናስ ከሥልጣኑ ይወርዳል ማለት ነው።

*23፥1-18፤* ሕዝ 26፥1-28፥19፤ አሞ 1፥9-10 ይመ።

23፥1 *ንግር፤* የ13፥1 ማብ ይመ። *ጢሮስ፤* በፊንቄ ጠረፍ ላይ ያለ ዋና ወደብ ሲሆን፣ ከቀርሜሎስ ተራራ በስተ ሰሜን 56 ኪሎ ሜትር ያህል ርቆ ይገኛል። ከፊል ከተማዋ 1ኪ.ሜ ርቀት ላይ በሁለት ድንጋያማ ደሴቶች ላይ የተሠራ ነበር። የጢሮስ ንጉሥ ኪራም ለቤተ መቅደሱ ሥራ ዝግባና ሠራተኞችን ልኮ ነበር (1ነገ 5፥8-9)፤ የንጉሥ ሰሎሞንን የንግድ መርከቦች የሚያንቀሳቅሱ ባለሙያዎችም ተልከው ነበር (1ነገ 9፥27)። *መርከቦች ሆይ፤ ዋይ በሉ፤* ቍ 14 ይመ። *የተርሴስ መርከቦች፤* የንግድ መርከቦች (የ2፥16 ማብ ይመ) ናቸው። *ተደምስሳለች፤* ይህ ትንቢት በአሦር፣ በናቡከደነፆርና በእስክንድር አማካይነት ተፈ

ከቆጵሮስ ምድር፣
  ዜናው ወጥቶላቸዋል።

[2]እናንት የባሕር ተጓዦች ያበለጠጓችሁ፣
  በደሴቲቱ የምትኖሩ፣
  የሲዶና ነጋዴዎችም ጸጥ በሉ።
[3]በታላላቅ ውሆች ላይ፣
  ለጢሮስ የሺሖር እህል ይመጣላት ነበር፤
የዐባይ መከር[c] ገቢዋ ነበር፤
  እርሷም የመንግሥታቱ የንግድ መናኸሪያ
    ሆነች።
[4]አንቺ ሲዶና ሆይ፣
  አንቺ የባሕር ምሽግ ሆይ፣ ዕፈሪ፤
ባሕሩ፣ "አላማጥሁም፤ አልወለድሁም፤
  ወንዶችና ሴቶች ልጆችን አላሳደግሁም"
    ብሎአልና።
[5]ከጢሮስ የሚመጣው ዜና፣
  በግብፅ በሚሰማበት ጊዜ ጭንቅ ይይዛቸዋል።

[6]እናንት በደሴቲቱ የምትኖሩ፣ በዋይታ አልቅሱ፤
  ወደ ተርሴስም ተሻገሩ፤
[7]እግሮቿ ሩቅ አገር የወሰዷት፣
  በዚያም እንድትሰፍር ያደረጓት፣
ጥንታዊቷ የድሮ ከተማ፣
  የተድላ የደስታ ከተማችሁ ይህች ናትን?
[8]አክሊል በምታቀዳጀዋ፣
  ነጋዴዎቿ መሳፍንት በሆኑ፣
በምድር የከበሩ ሻጮችና ለዋጮች በነበሯት፣
  በጢሮስ ላይ ይህን ያሰበ ማን ነበር?
[9]የክብርን ሁሉ ትዕቢት ሊያዋርድ፣
  በምድር ከፍ ከፍ ያለውንም ሁሉ ዝቅ
    ሊያደርግ፣
  የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ወስኖአል።
[10]የተርሴስ ልጅ ሆይ፤
  ከእንግዲህ የሚከለክልሽ የለምና
  እንደ ዐባይ ወንዝ ምድርሽን አጥለቅልቂ።

23፥2 መሳ1፥31፤ ኢዮ2፥13፤ሕዝ27፥5-24
23፥3 ዘፍ41፥5፤ መዝ83፥7፤ኢሳ19፥7
23፥4 ዘፍ10፥15፡ 19፤ኢሳ54፥1
23፥5 ሕዝ26፥17-18፤ 30፥9
23፥6 ዘፍ10፥4
23፥7 ቊ12፤ ኢሳ5፥14፤21፥5፤ 32፥13፤ሕዝ26፥13
23፥8 ሕዝ28፥5፤ ናሆ3፥16፤ራእ18፥23
23፥9 ኢዮ40፥11፤ ኢሳ5፥13፤9፥15፤ 13፥11፤14፥24፤ ሕዝ27፥3
23፥11 ቊ14፤ ዘፀ14፥21፤መዝ46፥6፤ ኢሳ25፥2፤ሕዝ26፥4፤ ዘካ9፥3-4
23፥12 ቊ7፤ ዘፍ10፥4፤ኢሳ37፥22፤ 47፥1፤ኤር14፥17፤ 46፥11፤ሰቆ2፥13፤ ሶፎ3፥14፤ዘካ2፥10፤ ራእ18፥22
23፥13 2ነገ25፥1፤ መዝ74፥14፤ኢሳ10፥5፡ 7፤18፥6፤43፥14፤ ኤር51፥12
23፥14 ቊ11፤ ዘፍ10፥4፤1ነገ10፥22፤ ኢሳ2፥16
23፥15 መዝ90፥10፤ ኤር25፥22
23፥16 ምሳ7፥10
23፥17 ዘዳ23፥17-18፤ መዝ90፥10፤ ኤር25፥26፤ ሕዝ16፥26፤ናሆ3፥4፤ ራዕ17፥1፤18፥3፡9

[11]*እግዚአብሔር* እጁን በባሕር ላይ ዘረጋ፤
  መንግሥታቷንም አስደነገጠ፤
የከነዓንም[d] ምሽጎች እንዲፈርሱ፣
  ትእዛዝ ሰጠ፤
[12]እንዲህም አለ፤ "አንቺ የተቀጠቀጥሽ የሲዶን
    ድንግል ሆይ!
  ከእንግዲህ ደስ አይበልሽ፤

"ተነሺ ወደ ቆጵሮስ ተሻገሪ፤
  በዚያም እንኳ ሰላም አታገኚም።"
[13]እነሆ፤ የባቢሎናውያንን[e] ምድር ተመልከቱ፤
  ሕዝቡ ከንቱ ሆኖአል።
አሦራውያን የምድረ በዳ አራዊት
  መፈንጫ አደረጓት፤
የግንብ ማማቸውን ሠሩባት፤
  ምሽጎቿን አወደሙ፤
  የፍርስራሽ ክምር አደረጓት።

[14]እናንት የተርሴስ መርከቦች፣ ዋይ በሉ፤
  ምሽጋችሁ ፈርሶአል።

[15]በዚያ ጊዜ ጢሮስ፣ የአንድ ንጉሥ የሕይወት ዘመን ያህል፣ ለሰባ ዓመታት ትረሳለች። ከሰባ ዓመት በኋላ ግን፣ ስለ ጋለሞታዪቱ የተዘፈነው በጢሮስ ላይ ይሆናል፤

[16]"አንች የተረሳሽ ጋለሞታ፤
  በገና አንሺ፤ በከተማዪቱ ውስጥ ዙሪ፤
እንድትታወሽም፣
  በገናሽን አሳምረሽ ምቺ፤ ብዙ ዘፈን
    ዝፈኚ።"

[17]ሰባው ዓመት ካለፈ በኋላ *እግዚአብሔር* ጢሮስን ይጐበኛታል፤ ወደ ቀድሞው የግልሙትና ሥራዋ ተመልሳ፣ በምድር ላይ ካሉት

[c]2:3 የማሶሬቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ አንድ የሙት ባሕር ቅጅ ግን፣ *ሲዶን /በባሕሩ ላይ የምትሻገሪ/ ተጓዦችሽ* [3]*በታላቁ ባሕር ላይ የሆኑ/ የሺሖር እህል/ የዐባይ መከር* ይላል።
[d]11 አንዳንድ ቅጆች፣ *ፊንቄ* ይላሉ።
[e]13ወይም፣ *ከለዳውያን*

ጽሞአል። ናቡከደነፆር በ572 ዓ.ቅ.ክ ላይ የከተማዪቱን ቍልፍ ቦታ ያዘ (ሕዝ 26፥7-11 ይመ)፤ የደሴቲቱ ምሽግ የተያዘው ግን ዓ.ቅ.ክ በ332 ላይ በታላቁ እስክንድር ነው (ከሕዝ 26፥3-5 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቆጵሮስ፤* ከጢሮስ ጋር የቅርብ ግንኙነት ያላት ደሴት ናት (ሕዝ 27፥6 ይመ)።

23፥2፡4፡12 *ሲዶና፤* ሕዝ 28፥20-26 ይመ፤ የታወቀች ሌላዋ የፊንቄ ከተማ ስትሆን፣ ከጢሮስ በስተ ሰሜን 40 ኪ.ሜ ያህል ርቃ ትገኛለች።

23፥2 *የባሕር ተጓዦች ... ነጋዴዎች፤* የጢሮስ የንግድ እንቅስቃሴ በመላው የሜድትራኒያን አካባቢ ከፍተኛ ለውጥ አምጥቶአል (ቍ 3፡8 ይመ)።

23፥3 *ሺሖር፤* ምናልባት የዐባይ ወንዝ ምሥራቅ ቅርንጫፍ ሳይሆን አይቀርም (ኤር 2፥18 ይመ)። *የዐባይ መከር፤* 19፥7 እና ማብ ይመ።

23፥4 *የባሕር ምሽግ፤* ጢሮስ ነው (የቍ 1 ማብ ይመ)። *አላማጥሁም አልወለድሁም፤* ከ54፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

23፥6 *ተርሴስ፤* ምናልባት በስፓኝ ያለው ጠርጤስስ (ዮና 1፥3 እና ማብ ይመ)፣ ወይም በምዕራብ ሜድትራኒያን ያለ ደሴት፣ አሊያም በሰሜን አፍሪካ ጠረፍ የሚገኝ ስፍራ ሊሆን ይችላል።

23፥7 *ሩቅ አገር ... እንድትሰፍር፤* በሰሜን አፍሪቃ የምትገኘው ካርታጎ የጢሮስ ቅኝ ግዛት ነበረች፤ ስለዚህ ጠርሴስም ሌላዋ ልትሆን ትችላለች። *ጥንታዊቷ የድሮ ከተማ፤* ጢሮስ የተመሠረተችው ከ2000 ዓ.ቅ.ክ በፊት ነበር። *የደስታ፤* የ22፥2 ማብ ይመ።

23፥8-9 *ያሰበ፤* 14፥24፡26-27፤ 25፥1 ይመ።

23፥8 *አክሊል በምታቀዳጀዋ፤* ጢሮስ በግዛቶቿ ላሉት ነገሥታት ዘውድ ትጭንላቸው ነበር። *ነጋዴዎቿ ... የከበሩ፤* ሕዝ 28፥4-5 ይመ።

23፥9 *የክብርን ሁሉ ትዕቢት፤* ሕዝ 27፥3-4 ይመ።

23፥10 *የተርሴስ ልጅ፤* ተርሴስንና ነዋሪዎቿ በሰው መስሎ ለማቅረብ የገባ ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው።

23፥11 *እጁን ... ዘረጋ፤* የ14፥26-27 ማብ ይመ። *ከነዓን፤* ምናልባት ይህ ስፍራ፣ "ፊንቄ" ወይም የዛሬዪቱን ሊባኖስ በከፊል የሚያመለክት ይሆናል።

23፥12 *የሲዶን ድንግል፤* የቍ 10 ማብ ይመ። *የተቀጠቀጥሽ፤* ሲዶና በሰባተኛው መቶ ዓ.ቅ.ክ ላይ በአስራዶን ተይዛ ነበር፤ በኋላም በ587 ዓ.ቅ.ክ ገደማ በናቡከደነፆር ተያዘች (ከኤር 25፥22 ጋር ያነጻጽሩ)።

23፥13 *አሦራውያን፤* ሰናክሬም በ689 ዓ.ቅ.ክ ላይ የባቢሎንን ከተማ ደመሰሰ። ፊንቄም የዚያን ጊዜዋን ባቢሎን ትመስል ነበር። *የምድረ በዳ አራዊት፤* ከ13፥21ጋር ያነጻጽሩ። *ማማቸውን ሠሩባት፤* የ2ነገ 25፥1 ማብ ይመ።

*23፥14፤* ቍ 1 እና ማብ ይመ።

23፥15 *ሰባ ዓመታት፤* እስራኤላውያን በባቢሎን ምርኮ የሚቈዩበት ጊዜና (ኤር 25፥11፤ 29፥10 ይመ) ሰናክሬም ባቢሎን ተደመሰሰ ትቀራለች በማለት ዐዋጅ ያስነገረበት ዘመን ርዝመት አንድ ነው።

*23፥16፤* ከምሳ 7፥10-15 ጋር ያነጻጽሩ።

23፥17 *ወደ ቀድሞው የግልሙትና ሥራዋ ተመልሳ ... ትገለሙታለች፤* "የምትገለሙት" አገር ማለት በዘመኑ ብቻ በምንም ይሁን በምን ትርፍ ለማግበስበስ ስትል የምትራወጥ ናት፤ መንገዱም ራስን በርኵሰት ማስደሰት ብቻ ነው (ከራእ 17፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

የዓለም መንግሥታት ሁሉ ጋር በንግዷ ትገለሙታለች። 18ያም ሆኖ ትርፏና ያገኘችው ሁሉ ለእግዚአብሔር የተለየ ይሆናል፤ አይከማችም፤ አይጠራቀምም። ትርፏም በእግዚአብሔር ፊት ለሚኖሩት የተትረፈረፈ ምግብና ጥሩ ልብስ ይሆናል።

## እግዚአብሔር ምድርን ፈጽሞ ያጠፋታል

24 እነሆ፤ እግዚአብሔር ምድርን ባድማ ያደርጋታል፤
ፈጽሞ ያጠፋታል፤
የፍርስራሽ ክምር ያደርጋታል፤
ነዋሪዎቿንም ይበትናል።
2ነገሩ ሁሉም አንድ ዐይነት ይሆናል፤
በሕዝቡ ላይ የሚሆነው በካህኑ፣
በአገልጋዩ ላይ የሚሆነው በጌታው፣
በአገልጋይዋ ላይ የሚሆነው በእመቤቷ፣
በገዢው ላይ የሚሆነው በሻጩ፣
በተበዳሪው ላይ የሚሆነው በአበዳሪው፣
በብድር ከፋይ ላይ የሚሆነው በብድር ሰጪው ይሆናል።
3ምድር ፈጽሞ ባድማ ትሆናለች፤
ጨርሶም ትበዘበዛለች፤
እግዚአብሔር ይህን ቃል ተናግሮአልና።
4ምድር ትደርቃለች፤ ትረግፋለች፤
ዓለም ትዝላለች፤ ትረግፋለች፤
የምድርም መሳፍንት ይዝላሉ።
5ምድር በሕዝቧ ትረክሳለች፤
ሕግን ጥሰዋል፤
ሥርዐትን ተላልፈዋል፤
ዘላለማዊውንም ኪዳን አፍርሰዋል።
6ስለዚህ ርግማን ምድርን ትበላለች፤
ሕዝቦቿም ስለ በደላቸው ይቀጣሉ፤
ስለዚህ የምድር ነዋሪዎች ተቃጥለዋል፤
በጣም ጥቂት የሆኑት ቀርተዋል።
7አዲሱ የወይን ጠጅ ዐለቀ፤ የወይኑም ተክል ደረቀ፤
ደስተኞችም ሁሉ አቃሰቱ።
8የከበሮ ደስታ ጸጥ አለ፤
የጨፋሪዎች ጩኸት አበቃ፤
ደስ የሚያሰኘውም በገና ርጭ አለ።
9ከእንግዲህ እየዘፈኑ የወይን ጠጅ አይጠጡም፤
መጠጡም ለሚጠጡት ይመሯል።
10የፈራረሰችው ከተማ ባድማ ሆነች፤
የየቤቱም መግቢያ ተዘጋ።
11በየአደባባዩ የወይን ጠጅ ያለህ እያሉ ይጮኻሉ፤
ደስታው ሁሉ ወደ ሐዘን ይለወጣል፤
ሐሤቱም ሁሉ ከምድር ገጽ ጠፍቶአል።
12ከተማዪቱ ፈጽማ ፈርሳለች፤
በሮቿም ደቀው ወድቀዋል።
13የወይራ ዛፍ ሲመታ፣
የወይንም ዘለላ ሲቈረጥ ቃርሚያ እንደሚቀር ሁሉ፣
በምድሪቱ ላይ፣
በሕዝቦችም ላይ እንዲሁ ይሆናል።
14ድምፃቸውን ከፍ ያደርጋሉ፤ በደስታም ይጮኻሉ፤
ከምዕራብም የእግዚአብሔርን ክብር ያስተጋባሉ።
15ስለዚህ በምሥራቅ ለእግዚአብሔር ክብር ስጡ፤
ከባሕር ደሴቶችም፣
የእስራኤልን አምላክ የእግዚአብሔርን ስም ከፍ ከፍ አድርጉ።
16"ለጻድቁ ክብር ይሁን" የሚል ዝማሬ፣
ከምድር ዳርቻ ሰማን፤
እኔ ግን፣ "ከሳሁ፤ መነመንሁ፤
ወዮልኝ!

23፥18 ዘፀ28፥36፤ 39፥30፤ኢሱ6፥17-19፤ መዝ72፥10፤ ኢሳ18፥7፤60፥5-9፤61፥6፤አሞ1፥9-10፤ሚክ4፥13፤ዘካ14፥1፡14
24፥1 ቁ 20፤ ዘፍ11፥9፤ኢሱ6፥17፤ ኢሳ2፥19-21፤13፥5፤ 33፥9፤ኤር25፥29
24፥2 ዘሌ25፥35-37፤ ዘዳ23፥19-20፤ኢሳ3፥1-7፤ ሕዝ7፥12፤ሆሴ4፥9፤ 1ቆሮ7፥29-31
24፥3 ዘፍ6፥13፤ ኢሳ6፥11-12፤7፥7፤10፥6
24፥4 ኢሳ2፥12፤ 3፥26፤15፥6፤ኤር12፥11፤14፥4፤ኢዩ1፥10
24፥5 ዘፍ3፥17፤ 9፥11፤ኢሳ1፥2፤ 9፥17፤10፥6፤59፥12፤ ኤር7፥28፤11፥10
24፥6 ኢሱ23፥15፤ ኢሳ1፥31
24፥7 ኢሳ3፥26፤ 7፥23፤15፥6፤16፥8-10፤ 32፥10፤ኤር48፥33፤ ኢዩ1፥5
24፥8 ዘፍ31፥27፤ መዝ137፥2፤ኢሳ5፥12፡14፤21፥5፤ኤር7፥34፤ 16፥9፤25፥10፤33፥11፤ ሰቆ5፥14፤ሕዝ26፥13፤ ሆሴ2፥11፤ራእ18፥22
24፥9 ኢሳ5፥11፡20፡22
24፥10 ዘፍ1፥2፤ ኢሳ6፥11፤25፥2፤ 26፥5
24፥11 መዝ144፥14፤ ኢሳ15፥6፤16፥10፤ 32፥13፤ኤር14፥3፤ ሰቆ2፥12
24፥12 ኢሳ3፥26፤ 13፥2፤19፥18
24፥13 ዘዳ30፥4፤ ኢሳ17፥6፤አብ1፥5፤ ሚክ7፥1
24፥14 ኢሳ12፥6፤ 43፥5፤49፥12 24፥15 ዘፀ5፥2፤መዝ113፥3፤ ኢሳ11፥11፤12፥4፤25፥3፤42፥12፤59፥19፤66፥19፤ሚል1፥11፤ 2ተሰ1፥12 24፥16 ዘሌ26፥39፤1ሳሙ4፥8፤ዕዝ9፥15፤መዝ25፥3፤ 48፥10፤ 65፥8፤ኢሳ5፥8፤ 21፥2፤28፥5፤33፥1፤60፥1፡19፤ኤር3፥6፡20፤ 5፥11፤9፥2፤10፥19፤45፥3፤ሆሴ5፥7፤ 9፥1፤

23፥18 *ለእግዚአብሔር የተለየ፤* በግልሙትና የተገኘ ሀብት ለእግዚአብሔር ስጦታ መቅረብ የለበትም (ዘዳ 23፥18)፣ ለጥፋት የተዘጋጀው ወርቅና ብር ግን (የዘዳ 2፥34 ማብ ይመ)፣ በእግዚአብሔር ግምጃ ቤት ይቀመጣል (ኢሱ 6፥17፡19 ይመ፤ ከሚክ 4፥13 ጋር ያነጻጽሩ)። *በእግዚአብሔር ፊት ለሚኖሩት፤* እስራኤላውያን አንድ ቀን የአሕዛብን ብልጽግና ይቀበላሉ (የ18፥7 ማብ ይመ፤ ከ60፥5-11፤ 61፥6 ጋር ያነጻጽሩ)።

*24፥1-27፥13፤* ከምዕራፍ 24-27 ያለው የመጨረሻውን ዘመን ፍርድና በረከት የሚመለከት ሲሆን፣ እግዚአብሔር በክፉ ኀይላት ላይ የሚቀዳጀውን የመጨረሻ ድል ጊዜ ያሳያል። ከምዕራፍ 34-35 ያለው ክፍል ከምዕራፍ 28-33 ላለው ማጠቃለያ እንደ ሆነ ሁሉ፣ እነዚህም ምዕራፎች ከምዕራፍ 13-23 ላለው ክፍል ማጠቃለያ ናቸው።

24፥1 *ምድርን ባድማ ያደርጋታል፤* ከ2፥10፡19፡21 ጋር ያነጻጽሩ፤ 13፥13 እና ማብ ይመ። *ነዋሪዎቿንም ይበትናል፤* ዘፍ 11፥9 ይመ።

*24፥2፤* የማኅበራዊ ኑሮ ልዩነቶች ከእግዚአብሔር ፍርድ አያድኑም (ከ3፥1-3 ጋር ያነጻጽሩ)።

24፥4 *ትደርቃለች፤ ትረግፋለች፤* ሞዓብን በተመለከተ በ15፥6፤ 16፥8 የተጠቀሱ ቃሎች ናቸው፤ ከ34፥4 ጋር ያነጻጽሩ።

24፥5 *ዘላለማዊውንም ኪዳን አፍርሰዋል፤* ነገሩ በዘፍ 9፥8-17 የተጠቀሰውን ቃል ኪዳን የሚያመለክት ይመስላል (ዘፍ 9፥11 እና ማብ ይመ) ቊ 18 እና ማብ ይመ። ቃል ኪዳን ከመለኮት አንጻር ሲታይ ዘላለማዊ መሆኑ ባያጠራጥርም ኀጢአተኛው የሰው ልጅ ሊያፈርሰው ይችላል።

24፥6 *ርግማን፤* ክፋት በዓለም ላይ ከመብዛቱ የተነሣ፣ ፈጽሞ የሚያጠፋው የእግዚአብሔር ቊጣ ርግማን የምድርን ነዋሪዎች ሁሉ ያቃጥላቸዋል (ከዘፍ 8፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ፤ ከዘፍ 9፥8-17 ኪዳን ጋርም ያነጻጽሩ)።

24፥7 *የወይኑም ተክል ደረቀ፤* ቊ 4 እና ማብ ይመ።

24፥8 *ደስታ ጸጥ፤* ከ22፥2፡13፤ 23፥7 ጋር ያነጻጽሩ።

24፥9 *እየዘፈኑ የወይን ጠጅ፤* በ5፥11-13 ላይ የተጠቀሰው የይሁዳም ባሕርይ እንዲሁ ነበር (የዚያኑ ማብ ይመ)።

24፥10 *የፈራረሰችው ከተማ፤* በ25፥2፤ 26፥5፤ 27፥10 ላይ ተመሳሳይ ሐሳብ ቀርቦአል (ከ17፥1፤ 19፥18 ጋር ያነጻጽሩ)። ባቢሎንን፣ ጢሮስን፣ ኢየሩሳሌምንና ሮምን በመሰሉ እግዚአብሔርን በተቃወሙ ከተሞች ላይ የመጣውን ፍርድ የሚያመለክት ነው።

*24፥13፤* የሚቀረው ጥቂት የወይራ ዛፍና የወይን ተክል ብቻ ነው (ቊ 6፤17፥6፡11 ይመ)።

24፥14 *ድምፃቸውን፤* እግዚአብሔርን የሚፈሩ ከፍርድ ያመለጡ ናቸው።

24፥15 *ደሴቶችም፤* የ11፥11 ማብ ይመ።

24፥16 *ከምድር ዳርቻ፤* የ11፥12 ማብ ይመ። ምናልባት የእግዚአብሔርን ሕዝብ ለመደምሰስ አጥብቀው በሚሹ ከዳተኛ ሕዝቦች ክፋት የተነሣ የሚጠፉ፣ ፈሪሀ እግዚአብሔር ያደረበትን ማኅበረ ሰብ በጥቅሉ የሚወክል ሳይሆን አይቀርም። *ከሳሁ ... አሳልፈው ሰጡ፤* በዕብራይስጡ ቅጅ በዚህ ጥቅስ ላይ የሚገኙት የመጨረሻዎቹ አራት ስንኞች ውስጥ በተደጋጋሚ የተጠቀሱት ቃላት ለሥነ ጽሑፉ ልዩ ውበት ሰጥተውታል። *ወዮልኝ፤* ኢሳይያስ በ6፥5 ላይ የገለጸውን የሚመስል ስሜት አለው።

ከዳተኞች አሳልፈው ሰጡ፤
ከዳተኞች በክሕደታቸው አሳልፈው ሰጡ"
አልሁ።
[17]በምድር የምትኖር ሕዝብ ሆይ፤
ሽብር፣ ጕድጓድና ወጥመድ ይጠብቁሃል።
[18]ከሽብር ድምፅ የሚሸሽ፣
ወደ ጕድጓድ ይገባል፤
ከጕድጓድ የወጣም፣
በወጥመድ ይያዛል።
የሰማይ መስኮቶች ተከፍተዋልና፤
የምድርም መሠረት ተናወጠ።
[19]ምድር ተከፈለች፤
ምድር ተሰነጠቀች፤
ምድር ፈጽማ ተናወጠች።
[20]ምድር እንደ ሰካራም ዞረባት፤
ነፋስ እንደሚወዘውዘውም ጎጆ ሆነች፣
የዐመጿ ሸክም ከባድ ስለ ሆነ ትወድቃለች፤
እንደ ገናም አትነሣም
[21]በዚያ ቀን እግዚአብሔር፣
በላይ በሰማያት ያሉትን ኀይሎች፣
በታችም በምድር ያሉትን ነገሥታት
ይቀጣቸዋል።
[22]በጕድጓድ ውስጥ እንዳሉ እስረኞች፣
በአንድ ላይ ይታጐራሉ፤
በእስር ቤት ይዘጋባቸዋል[+]፣
ከብዙ ቀንም በኋላ ለፍርድ ይቀርባሉ።
[23]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
በጽዮን ተራራና በኢየሩሳሌም፣
በሽማግሌዎቹም ፊት በክብሩ ይነግሣል፤
ጨረቃ ትሸማቀቃለች፤ ፀሓይም ታፍራለች።

### ምስጋና ለእግዚአብሔር

**25** እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ አምላኬ ነህ፤
ከፍ ከፍ አደርግሃለሁ፤ ስምህንም
አወድሳለሁ፤
አስቀድሞ የታሰበውን፣
ድንቅ ነገር፣
በፍጹም ታማኝነት አድርገሃልና።
[2]ከተማዪቱን የድንጋይ ክምር አድርገሃታል፤
የተመሸገችውንም ከተማ አፈራርሰሃታል፤
የተመሸገችው የባዕድ ከተማ ከእንግዲህ አትኖርም፤
ተመልሳም አትሠራም።
[3]ስለዚህ ብርቱ ሕዝቦች ያከብሩሃል፤
የጨካኝ አሕዛብ ከተሞችም ይፈሩሃል።
[4]ለድኻ መጠጊያ፣
በጭንቅ ጊዜ ለችግረኛ መጠለያ፣
ከማዕበል መሸሸጊያ፣
ከፀሓይ ትኵሳትም ጥላ ሆነሃል።
የጨካኞች እስትንፋስ፣
ከግድግዳ ጋር እንደሚላጋ ማዕበል ነውና፤
[5]እንደ ምድረ በዳም ትኵሳት ነው።
የባዕድን ጩኸት እረጭ ታደርጋለህ፤
ትኵሳት በደመና ጥላ እንደሚበርድ፣
የጨካኞችም ዝማሬም እንዲሁ ጸጥ ይላል።
[6]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር በዚህ ተራራ ላይ፣
ለሕዝብ ሁሉ ታላቅ የምግብ ግብዣ፣
የበሰለ የወይን ጠጅ ድግስ፣
ማለፊያ ጮማና ምርጥ የወይን ጠጅ ያዘጋጃል።
[7]በዚህም ተራራ ላይ፣
በሕዝብ ሁሉ ላይ የተጣለውን መጋረጃ፣
በመንግሥታት ላይ የተዘረጋውን መሸፈኛ
ያጠፋል፤
[8]ሞትንም ለዘላለም ይውጣል።
ጌታ እግዚአብሔር
ከፊት ሁሉ እንባን ያብሳል፤
የሕዝቡንም ውርደት
ከምድር ሁሉ ያስወግዳል፤

24፥17 ዘዳ32፥23-25፤ ኢሳ8፥14፤ኤር48፥43፤ ሉቃ21፥35
24፥18 ዘፍ7፥11፤ መሳ5፥4፤ኢዮ9፥6፤18፥9፤20፥24፤ መዝ11፥3፤ኢሳ8፥14፤ 42፥22፤ሰቆ3፥47፤ ሕዝ12፥13፤38፥19
24፥19 ዘዳ11፥6፤ መዝ46፥2
24፥20 ኢዮ12፥14፡ 25፤27፥18፤መዝ46፥2፤ ኢሳ1፥2፡28፤43፥27፤ 58፥1
24፥21 ኢሳ2፥11፡12፤ 10፥12፡20፤13፥11፤ ኤር25፥29፤1ቆሮ6፥3፤ ኤፌ6፥11-12፤ ራእ16፥14
24፥22 ኢሳ10፥4፤ 42፥7፡22፤ሕዝ38፥8፤ ሉቃ8፥31፤ራእ20፥7-10
24፥23 መዝ97፥1፤ ኢሳ2፥2፤13፥10፤ 28፥5፤41፥16፤45፥25፤ 60፥19፤ሕዝ48፥35፤ ዘካ2፥5፤ዕብ12፥22፤ ራእ21፥23፤22፥5
25፥1 ዘኍ23፥19፤ መዝ40፥5፤98፥1፤ 145፥2፤ኢሳ7፥13፤ 11፥5፤12፥1፡4፤ 14፥24፤37፥26፤ 46፥11፤ኢል2፥21፡ 26፤ኤፌ1፥11
25፥2 ዘዳ13፥16፤ ኢዮ12፥14፤ኢሳ13፥22፤ 17፥1፡3፤26፥5፤37፥26
25፥3 ዘዐ6፥2፤ መዝ22፥23፤ኢሳ11፥14፤ 13፥11
25፥4 2ሳሙ22፥3፤ መዝ55፥8፤118፥8፤ ኢሳ3፥14፤4፥6፤ 14፥30፤17፥10፤27፥5፤ 29፥5፡19፤33፥16፤ 49፥25፤ኢል3፥16
25፥5 መዝ18፥44፤ ኢሳ13፥11፤ ኤር51፥55
25፥6 ዘፍ29፥22፤ 1ነገ1፥25፤መዝ36፥8፤ምሳ9፥2፤ ኢሳ1፥19፤2፥2፤55፥1-2፤66፥11፤ኢል3፥18፤ማቴ8፥11፤22፥4፤ ራእ19፥9
25፥7 ኢዮ4፥9፤2ቆሮ3፥15-16፤ኤፌ4፥18
25፥8 ዘፍ30፥23፤መዝ119፥39፤ኢሳ7፥7፤15፥3፤26፥19፤30፥19፤ 35፥10፤51፥11፤65፥19፤ኤር31፥16፤ሆሴ13፥14፤ማቴ5፥11፤ 1ቆሮ15፥54-55፤1ጴጥ4፥14፤ራእ7፥14፡17፤21፥4

[+]22 ወይም፣ *ይለቀቃሉ*።

*ከዳተኞች፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ ጠላቶች ናቸው።

*24፥17-18፤* ከአሞ 5፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

24፥17 *ሽብር፣ ጕድጓድና ወጥመድ፤* በዕብራይስጡ ቅጅ በተደጋጋሚ የተጠቀሱ ተመሳሳይ ቃላት አሉ፤ የቍ 16 ማብ ይመ፤ የኤር 48፥43 ማብ ይመ።

24፥18 *የሰማይ መስኮቶች፤* በኖኅ ዘመን የነበረውን ጐርፍ ያስታውሳል (ዘፍ 7፥11፤ 8፥2)። *የምድርም መሠረት ተናወጠ፤* የመሬት መንቀጥቀጥንና ነጕድጓድን የሚያመለክት ነው (የ13፥13 ማብ ይመ፤ ከኢል 3፥16 ጋር ያነጻጽሩ)።

24፥20 *እንደ ሰካራም፤* ከ 19፥14 ጋር ያነጻጽሩ። *ጐጆ፤* 1፥8 እና ማብ ይመ።

24፥21 *በዚያን ቀን፤* የጌታ ቀን ነው (የ2፥11፡17፡20፤ 10፥20፡27 ማብ ይመ፤ ከ25፥9፤ 26፥1፤ 27፥1-2፡12-13 ጋር ያነጻጽሩ)። *በሰማያት ያሉትን ኀይሎች፤* ሰይጣንንና የወደቁትን መላእክት ያመለክታል (ኤፌ 6፥11-12 ይመ)።

24፥22 *በእስር ቤት ይዘጋባቸዋል፤* ከራእ 20፥2 ጋር ያነጻጽሩ። ከብዙ ቀናት በኋላ ለፍርድ ይቀርባሉ፤ ወይም ከእስር ቤት ይለቀቃሉ ማለት ነው፤ ከራእ 20፥7-10 ጋር ያነጻጽሩ።

24፥23 *በጽዮን ተራራ … ይነግሣል፤* 2፥2-4 እና ማብ ይመ። *ጨረቃ ትሸማቀቃለች፤ ፀሓይም ታፍራለች፤* በፍርድ ቀን ፀሓይና ጨረቃ ብርሃን አይሰጡም (የ13፥10 ማብ ይመ)፤ እግዚአብሔር ራሱ "የዘላለም ብርሃን" ነውና (60፥19-20፤ ከራእ 21፥23፤ 22፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

*25፥1-5፤* በምዕራፍ 24 ላይ ከተጠቀሰው ፍርድ ያመለጡ ያቀረቡት የምስጋና መዝሙር ነው (24፥14-16 እና ምዕራፍ 12 ይመ)።

25፥1 *አስቀድሞ የታሰበውን፤* 14፥24፡26-27፤ 23፥8-9 ይመ።

25፥2 *ከተማዪቱን … አፈራርሰሃታል፤* 24፥10 እና ማብ ይመ። *ተመልሳም አትሠራም፤* ከ24፥20 ጋር ያነጻጽሩ።

25፥3 *ብርቱ ሕዝቦች … የጨካኝ አሕዛብ፤* እንደ ግብፅና አሦር የመሳሰሉትን ያመለክታል (19፥18-25 እና ማብ ይመ)። *ያከብሩሃል፤ … ይፈሩሃል፤* 24፥15 ይመ።

25፥4-5 *መጠጊያ … መጠለያ… መሸሸጊያ … ጥላ፤* 4፥5-6 እና ማብ ይመ፤ ከ32፥2 ጋር ያነጻጽሩ።

*25፥6-8፤* ከክርስቶስ ዳግም ምጽአት በኋላ እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሚያደርገውን ግብዣ ያመለክታል።

25፥6-7፡10 *በዚህ ተራራ፤* የጽዮንን ተራራ የሚያመለክት ነው፤ 2፥2-4 እና ማብ ይመ፤ ከ24፥23 ጋር ያነጻጽሩ።

25፥6 *ግብዣ … ድግስ፤* ከንግሥ ሥርዐት (1ነገ 1፥25) ወይም ከሰርግ ሥርዐት ጋር (መሳ 14፥10) ይመሳሰላል፤ "ከበጉ ሰርግ እራት ግብዣ" ጋር ያነጻጽሩ (ራእ 19፥9)። *ታላቅ የምግብ ግብዣ፤* የታላቁ መንፈሳዊ በረከት ምሳሌ ነው (55፥2 ይመ)፤ *የበሰለ የወይን ጠጅ፤* በመጥመቂያው ውስጥ ለረጅም ጊዜ በመቀመጥ እጅግ ተወዳጅ የሆነ ማለት ነው (ኤር 48፥11፤ ሶፎ 1፥12 ይመ)።

25፥7 *የተጣለውን መጋረጃ … የተዘረጋውን መሸፈኛ፤* በሐዘን ጊዜ በተለይም የሞት አደጋ ሲያጋጥም ፊት የሚሸፈንበት ነው።

*25፥8፤* ይህ ጥቅስ በከፊል በ1ቆሮ 15፥54 ላይ ተጠቅሶአል። *ሞትንም … ይውጣል፤* ዋጭ የሆነው ሞት (መዝ 49፥14 እና ማብ ይመ) በመጨረሻ ራሱ ይዋጣል። *ጌታ እግዚአብሔር፤* 7፥7፤

*እግዚአብሔር* ተናግሮአልና።

[9]በዚያን ቀን እንዲህ ይባላል፤
"እነሆ፤ አምላካችን ይህ ነው፤
በእርሱ ታመንን፤ እርሱም አዳነን፤
*እግዚአብሔር* ይህ ነው፤ በእርሱ ታመንን፤
በማዳኑም ደስ ይበለን፤ ሐሤትም እናድርግ።"

[10]*የእግዚአብሔር* እጅ በዚህ ተራራ ላይ ያርፋል፤
ነገር ግን ጭድ ከጭቃ ጋር እንደሚረገጥ፣
ሞዓብም እንዲሁ ይረገጣል።
[11]ዋናተኛ ሲዋኝ እጁን እንደሚዘረጋ፣
በውስጡ ሆነው እጃቸውን ይዘረጋሉ፤
ጌታ በእጃቸው ተንኰል ሳይታለል፣
ትዕቢታቸውን ያዋርዳል።
[12]ከፍ ብሎ የተመሸገውን ቅጥርህን ዝቅ
ያደርገዋል፤
ወደ ታች ያወርደዋል፤
ወደ ምድር አውርዶም
ትቢያ ላይ ይጥለዋል።

የምስጋና መዝሙር

# 26

በዚያ ቀን ይህ መዝሙር በይሁዳ ምድር ይዘመራል፤
ብርቱ ከተማ አለችን፣
ስምሳካችን ቅጥሮቿንና ምሽጎቿን፣
ለድነት አድርጎአል።
[2]በእምነቱ የጸና
ጻድቅ የሆነ ሕዝብ ይገባ ዘንድ፣
በሮቿን ክፈቱ።
[3]በአንተ ላይ ታምናለችና፣
በአንተ የምትደገፈውን ነፍስ
ፈጽመህ በሰላም ትጠብቃታለህ።
[4]*በእግዚአብሔር* ለዘላለም ታመኑ፤
ጌታ *እግዚአብሔር* የዘላለም ዐምባ ነውና።
[5]በከፍታ የሚኖሩትን ዝቅ ዝቅ ያደርጋል፤
ከፍ ከፍ ያለችውን ከተማ ያዋርዳል፤
ወደ ምድር ይጥላታል፤
ከትቢያም ጋር ይደባልቃታል።
[6]እግር
የተጨቋኞች እግር፣
የድኾችም ኮቴ ይረግጣታል።
[7]የጻድቃን መንገድ ቅን ናት፤
አንተ ቅን የሆንህ ሆይ፤
የጻድቃንን መንገድ ታቃናለህ።
[8]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ በሕግህ[a] ጎዳና በመሄድ፣
አንተን ተስፋ አድርገናል፤
ስምህና ዝናህ፣
የልባችን ምኞት ነው።
[9]ነፍሴ በሌሊት ትናፍቅሃለች፤
መንፈሴም በውስጤ ትፈልግሃለች።
ፍርድህ ወደ ምድር በመጣ ጊዜ፣
የዓለም ሕዝቦች ጽድቅን ይማራሉ።
[10]ክፉዎች ርኅራኄ ቢደረግላቸው እንኳ፣
ጽድቅን አይማሩም፤
በቅንነት ምድር እንኳ ክፋትን ያደርጋሉ፤
*የእግዚአብሔርንም* ግርማ አያስተውሉም።
[11]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ክንድህ ከፍ ከፍ ብሎአል፤
እነርሱ ግን አላስተዋሉም፤
ለሕዝብህ ያለህን ቅናት ይዩ፤ ይፈሩም፤
ለጠላቶችህም የተዘጋጀው እሳት ይብላቸው።
[12]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ ሰላምን
መሠረትህልን፤
የሠራነውንም ሁሉ አንተ አከናወንህልን።
[13]*እግዚአብሔር* አምላካችን ሆይ፤
ከአንተ ሌላ ሌሎች ጌቶች ገዝተውናል፤
እኛ ግን የአንተን ስም ብቻ እናከብራለን።
[14]እነርሱ ሞተዋል፤ ከእንግዲህ በሕይወት
አይኖሩም፤
መንፈሳቸው ተነሥቶ አይመጣም።
አንተ ቀጣሃቸው፤ አጠፋሃቸው፤
መታሰቢያቸውንም ሁሉ ደመሰስህ።
[15]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ሕዝብን አበዛህ፤
ሕዝብን አበዛህ።

25፥9 ዘጸ32፥43፤ መዝ9፥2፤13፥5፤22፥5፤ 145፥19፤ ኢሳ2፥11፤ 9፥3፤10፥20፤12፥2፤ 19፥20፤33፥22፤ 35፥2፡4፡10፤40፥9፤ 41፥16፤43፥3፡11፤ 45፥15፡21፤49፥25-26፤ 51፥3፤60፥16፤ 61፥7፡10፤63፥8፤ 66፥14፤ኤር14፥8
25፥10 ዘኍ19፥37፤ ዘኍ21፥29፤ዘዳ23፥6፤ ኢሳ2፥2፤11፥14፤ አሞ2፥1-3
25፥11 ዘሌ26፥19፤ ኢዮ40፥12፤ኢሳ5፥25፤ 14፥26፤16፥14
25፥12 ኢዮ40፥11፤ ኢሳ2፥15፤15፥1፤ ኤር51፥44
26፥1 መዝ48፥13፤ ኢሳ10፥20፤14፥32፤ 30፥29፤32፥18፤ 60፥18፤ዘካ2፥5፤9፥8
26፥2 መዝ24፥3-4፡ 7፤85፥13፤ኢሳ1፥26፤ 4፥3፤9፥7፤50፥8፤ 53፥11፤54፥14፤58፥8፤ 62፥2
26፥3 1ዜና5፥20፤ ኢዮ22፥21፤መዝ22፥5፤ 28፥7፤ኢሳ9፥6፡7፤ 12፥2፤ፊል4፥7
26፥4 ዘፍ49፥24፤ መዝ62፥8፤ኢሳ12፥2፤ 50፥10
26፥5 ኢሳ25፥2፡ 12፤ሕዝ26፥11
26፥6 ኢሳ5፥5፤ 3፥15፤14፥30፤49፥26
26፥7 ዘዐ14፥19፤ መዝ25፥8፤26፥12፤ ኢሳ40፥4፤42፥16
26፥8 ዘጸ18፥18፤ መዝ1፥2፤37፥9፤ 130፥5፤145፥2፤ ኢሳ12፥4፤56፥1፤64፥5
26፥9 1ዜና16፥14፤ መዝ42፥1-3፤63፥1፤ 78፥34፤119፥55፤ ኢሳ55፥6፤ማቴ6፥33
26፥10 1ሳሙ12፥24፤ ኢሳ22፥12-13፤32፥6፤ 59፥7፡13፤ኤር2፥19፤ ሆሴ11፥7፤ማቴ5፥45፤የሐ5፥37-38፤ ሮሜ2፥4
26፥11 መዝ10፥12፤ ኢሳ1፥31፤9፥7፤18፥3፤44፥9፡18፤ኢል2፥18፤ ሚክ7፥16፤ዘካ1፥14፤ ዕብ10፥27
26፥12 መዝ68፥28፤119፥165፤ኢሳ9፥6
26፥13 ኢሳ2፥8፤10፥5፡11፤12፥4፤42፥8፤63፥7
26፥14 ዘዳ4፥28፤ ኢዮ26፥5፤መዝ9፥5፡6፤ ኢሳ10፥3
26፥15 ኢዮ12፥23፤ ኢሳ14፥2፤33፥17

[a]8 ወይም፣ *በፍርድህ* ተብሎ መተርጐም ይችላል

28፥16፤ 30፥15፤ 40፥10፤ 49፥22፤ 52፥4፤ 61፥11፤ 65፥13 ይመ። *ውርደት ... ያስወግዳል፤* 54፥4 ይመ።

*25፥9፤* ሌላው አጭር የምስጋና መዝሙር ነው። *በዚያን ቀን፤* 12፥1-4፤ 24፥21፤ 10፥20፡27 እና ማብ ይመ። *በእርሱ ታመንን፤ እርሱም አዳነን፤* ከመዝ 22፥4-5 ጋር ያነጻጽሩ። *ደስ ይበለን፤ ሐሤትም እናድርግ፤* ከ35፥10፤ 51፥11፤ 66፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

*25፥10-12፤* ስለ ፍርድ የተነገረውን የበለጠ ያብራራል።

25፥10 *ሞዓብ፤* በ34፥5-17 ላይ እንደ ተጠቀሰው ኤዶም፣ የእግዚአብሔርን ጠላቶች ሁሉ በምሳሌ ለመጥቀስ የገባ ነው፤ የ15፥1 ማብ ይመ።

25፥11 *ትዕቢታቸውን፤* የ16፥6 ማብ ይመ።

25፥12 *ከፍ ብሎ የተመሸገውን ቅጥርህን፤* ቊ 2፤ 2፥15፤ 2ሳ 3፥27፤ ኤር 51፥58 ይመ።

*26፥1-15፤* እግዚአብሔር ስላደረገው ትድግና ሌላው የምስጋና መዝሙር ነው።

26፥1 *በዚያ ቀን፤* 12፥1፡4፤ 24፥21፤ 25፥9 ይመ። የ10፥20፡27 ማብ ይመ። *ምሽጎቿን፤* ከዐፈር ወይም ከድንጋይ የተሠሩ ዕርዶች። (2ሳሙ 20፥15 ጋር ያነጻጽሩ)።

*26፥3፤* 30፥15 ይመ። *በአንተ ላይ ታምናለችና፤* ከመዝ 112፥6-8 ጋር ያነጻጽሩ። *በሰላም ትጠብቃታለህ፤* ከ25፥9 ጋር ያነጻጽሩ።

26፥4 *ዐምባ፤* 17፥10 እና ማብ ይመ።

26፥5 *ከፍ ከፍ ያለችውን ከተማ፤* የ24፥10 ማብ ይመ። *ከትቢያም ጋር ይደባልቃታል፤* ከ25፥2-12 ጋር ያነጻጽሩ።

26፥6 *የተጨቋኞች እግር፤* ጨቋኞች በ49፥24-26፤ 51፥22-23 ተዋርደዋል (ከ3፥14-15 ጋር ያወዳድሩ)።

26፥7 *መንገድ ቅን ናት፤ ... መንገድ ታቃናለህ፤* ይህ ፍሬ ሐሳብ በ40፥3-4፤ 42፥16፤ 45፥13 ይገኛል።

*26፥8፤* እግዚአብሔር ለእነርሱ ሲል የሚገልጸው ኀይሉ ነው (ሆሴ 12፥5-6 ይመ)። *ስምህና ዝናህ፤* ቊ 13፤24፥15፤25፥1 ይመ።

26፥9 *ፍርድህ፤* ቅጣት ማለት ነው (ከ 4፥4 ጋር ያነጻጽሩ)።

26፥10 *ርኅራኄ፤* የመከርን በረከትና አጠቃላይ ብልጥግናን ያመለክታል (ከማቴ 5፥45 ጋር ያነጻጽሩ)።

26፥11 *ክንድህ ከፍ ከፍ ብሎአል፤* የኀይል ምልክት ነው፤ 9፥12፡17፡21 እና ማብ ይመ፤ መዝ 89፥13 ይመ። *ቅናት፤* 9፥7 እና ማብ ይመ፤ ከ37፥32፤ 63፥15 ጋር ያነጻጽሩ። *እሳት፤* የ1፥31 ማብ ይመ።

26፥12 *ሰላምን፤* ቊ 3 ይመ።

26፥13 *ሌሎች ጌቶች፤* እንደ ግብፅ፣ እንደ አሦር ያሉትን ባዕዳን ገዦች ማለት ነው።

26፥14 *ሞተዋል፤ ... መንፈሳቸው ተነሥቶ አይመጣም፤* ይህን በ14፥9-10 ከተገለጸው ከባቢሎን ንጉሥ ዕጣ ፈንታ ጋር ያነጻጽሩ።

26፥15 *ሕዝብን አበዛህ፤* ይህ እውን የሚሆነው በ54፥2-3 እንደ ተገለጸው ከባቢሎን ምርኮ ከተመለሱ በኋላ ነው፤ ከ9፥3 ጋር ያነጻጽሩ።

ክብሩን ለራስህ አደረግህ፤
  የምድሪቱንም ወሰን ሁሉ አሰፋህ።
16እግዚአብሔር ሆይ፤ በተጨነቁ ጊዜ ወደ
    አንተ መጡ፤
  በገሥጽሃቸውም ጊዜ፣
  በለሆሳስ ድምፅ ይጸልያሉ†።
17እግዚአብሔር ሆይ፤ የፀነሰች ሴት ልትወልድ
    ስትል፣
  በምጥ እንደምትጨነቅና እንደምትጮኽ፣
  እኛም በፊትህ እንዲሁ ሆነናል።
18አረገዝን በምጥም ተጨነቅን፤
  ነገር ግን ነፋስን ወለድን፤
ለምድርም ድነትን አላመጣንም፤
  የዓለምን ሕዝብ አልወለድንም
19ነገር ግን ሙታንህ ሕያዋን ይሆናሉ፤
  በድናቸውም ይነሣል።
እናንት በዐፈር ውስጥ የምትኖሩ፣
  ተነሡ፤ በደስታም ዘምሩ።
ጠልህ እንደ ንጋት ጠል ነው፤
  ምድር ሙታንን ትወልዳለች።
20ሕዝቤ ሆይ፤ ሂድ ወደ ቤትህ ግባ፤
  በርህን ከኋላህ ዝጋ፤
ቍጣው እስኪያልፍ ድረስ፣
  ለጥቂት ቀን ተሸሸግ።
21በምድር ላይ የሚኖረውን ሕዝብ ስለ ኀጢአቱ
    ለመቅጣት፣
  እነሆ፤ እግዚአብሔር ከመኖሪያው ወጥቶ
    ይመጣል፤
ምድር በላይዋ የፈሰሰውን ደም ትገልጣለች፤
  የተገደሉትንም ከእንግዲህ አትሸሽግም።

## የእስራኤል ዐርነት መውጣት

**27** በዚያ ቀን እግዚአብሔር፣
  ተወርዋሪውን እባብ ሌዋታንን፣
የሚጠቀለለውን ዘንዶ ሌዋታንን
  በብርቱ፣ በታላቁና በኀይለኛ ሰይፍ
  ይቀጣዋል፤
  የባሕሩንም ግዙፍ አውሬ ይቈራርጠዋል።
2በዚያን ቀን እንዲህ ይባላል፤
  "ለመልካሙ የወይን ቦታ ዘምሩለት፤
3እኔ እግዚአብሔር ጠባቂው ነኝ፤
  ዘወትር ውሃ አጠጣዋለሁ፤
ስለዚህ ማንም አይጐዳውም፣
  ቀንና ሌሊት እጠብቀዋለሁ፤
4እኔ አልቈጣም።
  እሾኽና ኵርንችት ምነው በተነሡብኝ!
ለውጊያ በወጣሁባቸው፣
  አንድ ላይ ባቃጠልኋቸው!
5አለዚያ ይምጡና መሸሸጊያቸው ያድርጉኝ፤
  ከእኔ ጋር ሰላም ይፍጠሩ፤
  አዎን፤ ከእኔ ጋር ሰላም ያድርጉ።"
6በሚመጡት ቀናት ያዕቆብ ሥር ይሰዳል፤
  እስራኤልም ያቈጠቍጣል፤ ያብባልም፤
  በፍሬያቸውም ምድርን ሁሉ ይሞላሉ።
7የመቷትን እንደ መታቸው፣
  እግዚአብሔር እርሷንስ መታትን?
የገደሏትን እንደ ገደላቸው፣
  እርሷስ ተገደለችን?
8በጦርነትና በስደት ተፋለምሃት‡፤
  የምሥራቅ ነፋስ እንደሚነፍስበት ቀን፣
  በብርቱ ዐውሎ ነፋስ አሳደድሃት።
9ያዕቆብ የመሠዊያ ድንጋዮችን፣
  እንደ ኖራ ድንጋይ ፈጭቶ ሲያደቃቸው፣
የአሼራን ዐምድና የዕጣን መሠዊያዎችን፣
  ከቦታቸው ነቅሎ ሲጥል፣
  በዚያን ጊዜ በደሉ ይሰረይለታል፤

26፥16 መሳ6፥2፤ መዝ39፥11፤ኢሳ5፥30፤ 29፥4
26፥17 ኢሳ21፥3፤ ዮሐ16፥21፤ራእ12፥2
26፥18 ዘፍ49፥10፤ መዝ17፥14፤ ኢሳ33፥11፤42፥6፤ 49፥6፤51፥4፤59፥4፤ ኤር12፥16
26፥19 ዘፍ27፥28፤ መዝ22፥29፤ኢሳ18፥4፤ 25፥8፤66፥24፤ ሕዝ37፥1-14፤ ዳን12፥2፤ኤፌ5፥14
26፥20 ዘፀ12፥23፤ ኢዮ14፥13፤መዝ91፥1፡ 4፤ኢሳ10፥25፤30፥27
26፥21 ኢዮ16፥18፤ ኢሳ13፥9፡11፤18፥4፤ 29፥6፤30፥12-14፤ ሉቃ11፥50-51፤ ይሁ1፥14
27፥1 ቍ13፤ ዘፍ3፥24፤ዘዳ32፥41፤ ኢዮ3፥8፤26፥13፤ መዝ68፥30፤74፥13፤ ኢሳ2፥11፤28፥5፤ 31፥8፤34፥6፤65፥12፤ 66፥16፤ሕዝ21፥3፤ ናሆ3፥15፤ራእ12፥9
27፥2 ኢሳ5፥1፤ 24፥21፤ኤር2፥21
27፥3 መዝ91፥4፤ ኢሳ5፥2፤58፥11፤ ዮሐ6፥39
27፥4 ቍ11፤ ኢሳ10፥17፤ማቴ3፥12፤ ዕብ6፥8
27፥5 ኢዮ22፥21፤ መዝ119፥165፤ ኢሳ25፥4፤ሮሜ5፥1፤ 2ቆሮ5፥20
27፥6 ዘፍ40፥10፤ 2ነገ19፥30፤ መዝ72፥16፤ ኢሳ11፥1፡10፤ 37፥31፤ሕዝ17፥23፤ 36፥8፤ሆሴ14፥8
27፥7 ኢሳ10፥26፤ 11፥4፤37፥36-38
27፥8 ዘፍ41፥6፤ኢሳ49፥14፤50፥1፤54፥7
27፥9 ዘፀ23፥24፤34፥13፤ዘሌ26፥30፤ 2ዜና14፥5፤መዝ78፥38፤ ሮሜ11፥27

†16 በዕብራይስጡ የዚህ ሐረግ ትርጒም በትክክል አይታወቅም።
‡8 በዕብራይስጡ የዚህ ሐረግ ትርጒም በትክክል አይታወቅም።

*26፥16-18፤* ነቢዩ ኢሳይያስ በሕዝቡ ስም ለእግዚአብሔር የተናገረው ነው።

26፥16 *በተጨነቁ ጊዜ፤* በ5፥30፤ 8፥21-22 የተገለጸውን የአሦራውያንን ጭቈና የሚያመለክት ነው። የመሳፍንትም ዘመን ከዚሁ ጋር ይመሳሰላል (መሳ 6፥2፡6 ይመ)።

26፥17-18 በምጥ እንደምትጨነቅ፤ 13፥8እና ማብ ይመ፤ ከ37፥3 ጋር ያነጻጽሩ።

26፥18 *ለምድርም ድነትን፤* እስራኤል፣ "ለአሕዛብ ብርሃን" እንድትሆን ተመርጣለች (42፥6፤ 49፥6 እና ማብ ይመ፤ 9፥2 እና ማብ ይመ)።

*26፥19-21፤* ነቢዩ የእግዚአብሔርን የማረጋገጫ ቃል እንደ ገና ይናገራል።

26፥19 *ሙታንህ ሕያዋን ይሆናሉ፤ በድናቸውም ይነሣል፤* የእስራኤልን ተሐድሶ የሚያመለክት ሲሆን (ሕዝ 37፥11-12 ይመ)፣ የሙታንን ትንሣኤም ሳይመለከት አይቀርም (ዳን 12፥2)። ከ25፥8 ጋር ያነጻጽሩ፤ ከ26፥14 ጋር ያወዳድሩ። *ጠል፤* የፍሬያማነት ምሳሌ ነው (2ሳሙ 1፥21፤ ሆሴ 14፥5 ይመ)።

*26፥20-21፤* 24፥21-22 እና የ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ።

26፥20 *ቍጣው ... ለጥቂት ቀን፤* ከ10፥25፤54፥7-8 ጋር ያነጻጽሩ። ጭካኔ የሞላበት የአሦራውያን አገዛዝ፣ የባቢሎን ምርኮና ሌሎች ጭቈናዎች ሁሉ ያበቃሉ።

26፥21 *ለመቅጣት፤* 66፥14-16 ይመ። *ትገልጣለች ... ከእንግዲህ አትሸሽግም፤* የንጹሓኑ ሥጋና ደም፣ በጨቋኝ ኀይሎችም የታረዱት ጻድቃን በድን በምድር ተቀብሮ አይቀርም፤ ነገር ግን ወጥቶ በግልጽ በገዳዮቻቸው ላይ ይመሰክራል፤ እግዚአብሔርም ግድያውን በፍርዱ ይበቀላል (ዘፍ 4፥10 ይመ)።

27፥1-2፡12-13 *በዚያ ቀን፤* 10፥20፡27እና ማብ ይመ፤ እንደዚሁም 12፥1፡4፤ 24፥21፤ 25፥9፤ 26፥1 ይመ።

*27፥1፤* በከፍተኛ ደረጃ የተገለጸ የፍርድ ቃል ነው። *ሌዋታን ... አውሬ፤* ከከነዓናውያን አፈ ታሪክ የተወሰደ ሲሆን፣ እንደ ግብፅ ያሉ ክፉ መንግሥታት ምሳሌ ነው (30፥7 እና ማብ 51፥9፤ ሕዝ 29፥3፤ 32፥2 ይመ)። *ተወርዋሪውን እባብ... የተጠቀለለውን፤* ከኢዮ 3፥8፤ 41፥1፤ መዝ 74፥19 ጋር ያነጻጽሩ)። ስለ ሌዋታን የተጠቀሰው እንዲህ ዐይነቱ አገላለጽ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ይገኛል።

*27፥2-6፤* ሁለተኛው የወይኑ ቦታ መዝሙር (5፥1-7 እና ማብ ይመ)።

27፥2 *የወይን ቦታ፤* እስራኤልን ያመለክታል።

*27፥4-5፤* እንደ ሌሎች አሕዛብ ወይ "እሾኽና ኵርንችት" አልሆኑ ወይም ደግሞ በእግዚአብሔር አልታመኑ (29፥13 ይመ)፣ እስራኤል ከእግዚአብሔር ጋር ያላቸውን የለብታ ሕይወት ገልጦ ያሳያል።

27፥4 *እሾኽና ኵርንችት፤* 5፥6እና ማብ ይመ።

27፥6 *ሥር ይሰዳል፤* 11፥1፡10 እና ማብ ይመ። *ያቈጠቍጣል፤ ያብባልም፤* 4፥2 እና ማብ ይመ። የመሲሑ ዘመን እንደሚመጣም ያመለክታል። *ምድርን ሁሉ ይሞላሉ፤* ከ26፥18 ጋር ያነጻጽሩ።

*27፥7-11፤* እግዚአብሔር በኢሳይያስ ዘመን በእስራኤል ላይ የሚያመጣውን ፍርድ ያመለክታል።

27፥7 *የመቷትን?* ከ10፥24-26 ጋር ያነጻጽሩ።

27፥8 *በስደት፤* ምናልባት የባቢሎንን ምርኮ ማመልከቱ ይሆናል። *የምሥራቅ ነፋስ፤* ከምድረ በዳ የሚመጣው ሞቃት ነፋስ ነው (ኤር 4፥11፤ ሕዝ 19፥12 ይመ)።

27፥9 *የአሼራን ዐምድና የዕጣን መሠዊያዎችን፤* 17፥8 እና ማብ ይመ። *ፈጭቶ ሲያደቃቸው፤* ዘፀ 34፥13 ይመ። *ይሰረይለታል፤*

ይህም ኀጢአቱን የማስወገዱ ሙሉ ፍሬ
ይሆናል።
[10]የተመሸገባት ከተማ ባዶዋን ቀርታለች፤
እንደ ምድረ በዳም የተተወች ስፍራ ሆናለች፤
ጥጆች በዚያ ይሰማራሉ፤
እዚያም ይተኛሉ፤
ቅርንጫፎቿንም ልጠው ይበላሉ።
[11]ጫፎቿ ሲደርቁ ይሰበራሉ፤
ሴቶችም መጥተው ይማግዷቸዋል።
ማስተዋል የሌለው ሕዝብ ስለ ሆነ፣
ፈጣሪው አይራራለትም፤
ያበጀውም አይምረውም።

[12]በዚያ ቀን ከኤፍራጥስ ወንዝ እንሥቶ እስከ ግብፅ ደረቅ ወንዝ፣ እግዚአብሔር እህሉን ይወቃል፤ እናንተም የእስራኤል ልጆች ሆይ፤ አንድ በአንድ ትሰበሰባላችሁ። [13]በዚያ ቀን ታላቅ መለከት ይነፋል፤ በአሦር የጠፉትና በግብፅ የተሰደዱትም መጥተው፣ በተቀደሰው ተራራ በኢየሩሳሌም እግዚአብሔርን ያመልካሉ።

**ወዮ ለኤፍሬም**

**28** ለኤፍሬም ሰካራሞች የመታበያ አክሊል ለሆነች፣
በለመለመ ሸለቆ ዐናት ላይ ጕብ ብላ፣
የክብሩ ውበት ለሆነች ጠውላጋ አበባ፣
የወይን ጠጅ ለዘራቸው መኵራሪያ ለሆነች፣
ለዚያች ከተማ ወዮላት!
[2]እነሆ፤ ጌታ ኀያልና ብርቱ የሆነ ነገር
አለው፤
ይህም እንደ በረዶ ወጀብ፣ እንደሚያጠፋ
ዐውሎ ነፋስ፣
እንደ ኀይለኛ ማዕበል፣ እንደ ከባድ ዝናብ፣
በኀይል ወደ ምድር ይጥላታል።
[3]የኤፍሬም ሰካራሞች የመታበያ አክሊል፣
በእግር ይረገጣል።
[4]በለምለሙ ሸለቆ ዐናት ላይ ጕብ ብላ፣
የክብሩ ውበት የሆነች ጠውላጋ አበባ፣
ከመከር በፊት እንደ ደረሰች፣
ሰውም ድንገት አይቶ እንደሚቀጥፋት
ወዲያውኑም እንደሚውጣት በለስ
ትሆናለች።

[5]በዚያን ቀን የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ለተረፈው ሕዝቡ፣
የክብር ዘውድ፣
የውበትም አክሊል ይሆናል።
[6]እርሱም በፍርድ ወንበር ላይ ለሚቀመጠው፣
የፍትሕ መንፈስ፣
ጦርን ከከተማዪቱ በር ላይ ለሚመልሱም፣
የኀይል ምንጭ ይሆናል።

[7]እነዚህም በወይን ጠጅ ይንገዳገዳሉ፤
በሚያስክርም መጠጥ ይወላገዳሉ፤
ካህናቱና ነቢያቱ በሚያስክር መጠጥ
ተንገደገዱ፤
በወይን ጠጅ ነገር ተምታታባቸው፤
በሚያስክር መጠጥ ተወላገዱ፤
ራእይ ሲያዩ ይስታሉ፤
ፍርድ ሲሰጡም ይሰናከላሉ።
[8]የማዕድ ገበታቸው ሁሉ በትፋት ተሞልቶአል፤
ከትውኪያም የጸዳ ቦታ የለም።
[9]እነርሱም እንዲህ ይላሉ፤ "የሚያስተምረው
ማንን ነው?
መልእክቱን የሚያብራራውስ ለማን ነው?
ወተት ለተዉት ሕፃናት?
ወይስ ጡት ለጣሉት?
[10]በትእዛዝ ላይ ትእዛዝ፣ በትእዛዝ ላይ ትእዛዝ፤
በደንብ ላይ ደንብ፣ በደንብ ላይ ደንብ፤*
እዚህ ጥቂት፣ እዚያ ጥቂት ነውና።
[11]እንግዲያማ እግዚአብሔር፣

27፥10 ዘፍ1፥2፤ ዘዳ13፥16፤ኢሳ5፥5፡ 6፡17፤17፥2፤32፥14፤ ኤር10፥22፤26፥6፤ ሰቆ1፥4፤5፥18
27፥11 ቍ4፤ ዘዳ32፥18፡28፤ ኢሳ1፥3፤9፥17፤10፥33፤ 33፥12፤41፥8፤43፥1፡ 7፡15፤44፥1-2፡21፡24፤ ኤር11፥16
27፥12 ዘፍ15፥18፤ ዘዳ30፥4፤ኢሳ1፥9፤ 11፥12፤17፥6፤21፥10፤ ማቴ3፥12
27፥13 ቍ1፤ ዘፍ27፥29፤ዘሌ25፥9፤ መሳ3፥27፤መዝ22፥29፤ 86፥9፤106፥47፤ ኢሳ2፥2፤10፥19፤ 19፥21፡25፤ ማቴ24፥31
28፥1 ቍ3፡4፤ ዘሌ10፥9፤ኢሳ5፥11፤ 7፥2፤9፥9፤10፥5፤ 29፥1፤30፥1፤31፥1፤ 33፥1፤ሆሴ7፥5፤ አሞ6፥6
28፥2 ኢሱ10፥11፤ ኢሳ8፥7፤29፥6፤ 40፥10፤ዳን9፥26
28፥3 ቍ1፤ ኢዮ40፥12፤ኢሳ5፥5
28፥4 ቍ1፤ መሐ2፥13፤ሆሴ9፥10፤ ናሆ3፥12
28፥5 ኢሳ1፥9፤ 10፥20፤24፥16፡23፤ 27፥1፤29፥18፤30፥23፤ 62፥3፤ኤር13፥18፤ ሕዝ16፥12፤21፥26፤ ዘካ9፥16
28፥6 መሳ9፥44-45፤ 2ሳሙ14፥20፤ 2ዜና32፥8፤ኢሳ4፥4፤ 11፥2-4፤32፥1፡16፤ 33፥5፤ዮሐ5፥30
28፥7 ዘሌ10፥9፤ መዝ107፥27፤ኢሳ1፥1፤ 3፥12፤9፥15፤22፥13፤ 24፥2፤29፥11፤ ኤፌ5፥18
28፥8 ኤር48፥26
28፥9 ቍ26፤ መዝ32፥8፤131፥2፤ ኢሳ2፥3፤30፥20፤48፥17፤50፥4፤ 52፥7፤53፥1፤54፥13፤ኤር31፥34፤32፥33፤ ዕብ5፥12-13፤ 1ጴጥ2፥2
28፥10 ቍ13 28፥11 ዘፍ11፥7፤ኢሳ33፥19፤ኤር5፥15፤ሕዝ3፥5፤ 1ቆሮ14፥21

*10 በዚህና በቍጥር 13 ላይ ይብራይስጡ፣ *ፃቭ ፃቫቭ ፃቭ ፃቫቭ፣ ካቭ ቃካቭ ካቭ ለካቭ* ይላል፤ ምናልባት ትርጕም የለሽ ንግግርን ለማሳየት ይሆናል፤ ይኸውም የነቢያትን ቃል አስመስሎ መናገርን ሊሆን ይችላል።

እስራኤል (ያዕቆብ) በሚመጣው ፍርድ ኀጢአቱ ይሰረይለታል ማለት ነው።

27፥10 *የተመሸገባት ከተማ፤* ኢየሩሳሌም ናት። *ባዶዋን ... ሆናለች፤* ከ6፥11-12 ጋር ያነጻጽሩ። *ጥጆች በዚያ ይሰማራሉ፤* ከ5፥5፤ 7፥25 ጋር ያነጻጽሩ።

*27፥12-13፤* ከሚመጣው ፍርድ ባሻገር ያለውን የእግዚአብሔርን ማዳን ያመለክታል።

27፥12 *እህሉን ይወቃል፤* እስራኤላውያን በተበተኑባቸው አሕዛብ ላይ የሚመጣውን ፍርድ ያመለክታል (የ21፥10 ማብ ይመ)። ውቂያው እስራኤልን ከአሕዛብ ይለያል ማለት ነው። *ግብፅ ደረቅ ወንዝ፤* የተስፋዪቱ ምድር ደቡባዊ ወሰን የሆነ የኤል አሪሽ ጅረት ሳይሆን አይቀርም። የተስፋዪቱ ምድር ሰሜናዊ ወሰን የኤፍራጥስ ወንዝ ነው (ዘፍ 15፥18 እና ማብ፤ 1ነገ 4፥21፤ 8፥65 ይመ)።

27፥13 *ታላቅ መለከት፤* ብዙውን ጊዜ ወታደሮች እንዲሰበሰቡ ይነፋል (1ሳሙ 13፥3 ይመ)። *አሦር ... ግብፅ፤* 11፥11-12 እና ማብ ይመ። *በተቀደሰው ተራራ፤* የጽዮንን ተራራ ያመለክታል (2፥2-4 እና ማብ 24፥23፤ 25፥6-7፡10 እና ማብ ይመ)።

*28፥1-35፥10፤* ስድስት ተከታታይ ወዮታዎች (28፥1፤ 29፥1፤ 29፥15፤ 30፥1፤ 31፥1፤ 33፥1)፤ በአሕዛብ ላይ የተነገረውን ፍርድ (ም 34) እና የጽዮንን ደስታ የሚገልጠውን መዝሙር በማከተት (ም 35) ተብራርተውበታል። በምዕራፍ 5 ላይ ከተጠቀሱት ስድስት ወዮታዎች ጋር ያነጻጽሩ (የ5፥8-23 ማብ ይመ)።

28፥1 *ለኤፍሬም፤* የ7፥2 ማብ ይመ። *ሰካራሞች፤* የሰማርያ ከተማ በስምንተኛው መቶ ዓ.ቅ.ክ ተድላ ደስታ የሚፈጸምባት የፈንጠዝያ ከተማ ነበረች፤ 5፥11-13 እና ማብ፤ አሞ 6፥4-7 ይመ። *መታበያ፤* ቍ 3 እና የ16፥6 ማብ ይመ። *አክሊል፤* የሰሜኑ መንግሥት ዋና ከተማ የሆነችው ሰማርያ፣ ቢታወቀ ተራራ ላይ የተመሠረተች ውብ ከተማ ነበረች። *በለመለመ ሸለቆ* ከ5፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

28፥2 *ኀያልና ብርቱ፤* የአሦር ንጉሥ ነው። *በረዶ ወጀብ ... ዝናብ፤* ቍ 17፤ 8፥7-8 እና ማብ 17፥12 እና ማብ ይመ፤ ከ30፥30፤ 32፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

28፥5 *በዚያ ቀን፤* 4፥1-2፤10፥20፡27 እና ማብ 12፥1፡4፤ 24፥21፤ 25፥9፤ 26፥1፤ 27፥1-2፡12-13 ይመ። *የክብር ... የውበት፤* 4፥2 ይመ። *ለተረፈው፤* የ1፥9 ማብ ይመ።

28፥6 *የፍትሕ መንፈስ፤* 11፥2-4 እና ማብ ይመ። *በር፤* ከከተማዪቱ ለአደጋ እጅግ የተጋለጠ ቦታ ነው።

28፥7 *በወይን ጠጅ ... በሚያስክርም መጠጥ፤* የሃይማኖት መሪዎች በመጠጥ ሳይሆን፣ በመንፈስ ቅዱስ ሊሞሉ ይገባ ነበር፤ ዘሌ 10፥9፤ ዘኍ 11፥29፤ ኤፌ 5፥18 ይመ።

28፥8 *በትፋት፤* ከኤር 25፥16፡27 ጋር ያነጻጽሩ።

*28፥9-10፤* የኢሳይያስ አድማጮች በፌዝ መልክ የሚሰጡትን መልስ ያመለክታል፤ በ5፥19 ላይ ከተጠቀሰው የፌዝ ቃል ጋር ያነጻጽሩ።

*28፥11-12፤* በከፊል በ1ቆሮ 14፥21 ላይ ተጠቅሶአል።

በባዕድ ልሳን በእንግዳ ቋንቋ ለዚህ ሕዝብ
ይናገራል::
[12]እርሱ፣ “ይህቺ የዕረፍት ቦታ ናት፤ የደከመው
ይረፍ፤
ይህቺ የእፎይታ ቦታ ናት” ያለው ለማን
ነበር?
እነርሱ ግን መስማት አልፈለጉም::
[13]ስለዚህ *የእግዚአብሔር* ቃል፣
በትእዛዝ ላይ ትእዛዝ፣ በትእዛዝ ላይ ትእዛዝ፤
በደንብ ላይ ደንብ፣ በደንብ ላይ ደንብ፤
እዚህ ጥቂት እዚያ ጥቂት ይሆንባቸዋል::
ይህ የሚሆንባቸው ሄደው ወደ ኋላ እንዲወድቁ፣
እንዲቈስሉና በወጥመድ እንዲያዙ፣
እንዲማረኩም ነው::

[14]ስለዚህ በኢየሩሳሌም ያለውን ሕዝብ
የምትገዙ፣
እናንት ፌዘኞች *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ::
[15]እናንት፣ “ከሞት ጋር ቃል ኪዳን ገብተናል፤
ከሲኦልም ጋር ስምምነት አድርገናል፤
ውሸትን መጠጊያችን፣
ሐሰትን[ገ] መደበቂያችን አድርገናል፤
ታላቅ መቅሠፍት እየጠራረገ ሲያልፍ፣
ሊነካን አይችልም” በማለት ታብያችኋል::

[16]ስለዚህ ልዑል *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

“እነሆ፤ የተፈተነ ድንጋይ፣ የመሠረት ድንጋይ፣
ለጽኑ መሠረት የሚሆን የከበረ የማእዘን
ድንጋይ፣
በጽዮን አስቀምጣለሁ፤
በእርሱም የሚያምን አያፍርም::
[17]ፍትሕን የመለኪያ ገመድ፣
ጽድቅንም ቱንቢ አደርጋለሁ፤
ውሸት መጠጊያችሁን የበረዶ ዝናብ ይጠራ
ርገዋል
መደበቂያችሁንም ውሃ ያጥለቀልቀዋል::
[18]ከሞት ጋር የገባችሁት ቃል ኪዳን ይሻራል፤
ከሲኦልም ጋር ያደረጋችሁት ስምምነት
ይፈርሳል፤
ታላቁ መቅሠፍት እየጠራረገ ሲያልፍ፣
እናንተም ትጠራረጋላችሁ::

[19]በመጣ ቍጥር ይዞአችሁ ይሄዳል፤
ማለዳ ማለዳ፣ በቀንና በሌሊትም ይጠራርጋል::”

ይህን ቃል ብታስተውሉ፣
ሽብር በሽብር በሆነ ነበር::
[20]እግር ዘርግቶ እንዳይተኛ ዐልጋው አጭር ነው፤
ሰውነትንም ለመሸፋፈን ብርድ ልብሱ ጠባብ
ነው::
[21]*እግዚአብሔር* ሥራውን፣ አዎን ድንቅ ሥራውን
ሊሠራ፣
ተግባሩን፣ እንግዳ የሆነ ተግባሩን ሊያከናውን፣
በፐራሲም ተራራ እንዳደረገው ይነሣል፣
በገባዖን ሸለቆ እንዳደረገው ይነሣሣል::
[22]እንግዲህ ፌዛችሁን አቁሙ፤
አለዚያ እስራታችሁ ይጸናባችኋል፤
ጌታ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር*
መላውን ምድር ለማጥፋት ያወጀውን
ዐዋጅ ሰምቻለሁ::
[23]አድምጡ ድምፄን ስሙ፤
አስተውሉ ቃሌንም ስሙ::

[24]ገበሬ ሊዘራ መሬቱን ሲያዘጋጅ ያለማቋረጥ
ያርሳልን?
ጓሉን ሲከሰክስ፣ ዐፈሩን ሲያለሰልስ
ይከርማልን?
[25]ዕርሻውን አስተካክሎ፣
ጥቍር አዝሙድና ከሙን አይዘራምን?
ስንዴውንስ በትልሙ[ነ]፣
ገብሱን በተገቢ ቦታው፣
አጃውንም በተመደበው ስፍራ አይዘራምን?
[26]አምላኩ ያስተምረዋል፤
ትክክለኛውንም መንገድ ያሳየዋል::

[27]ጥቍር አዝሙድ በመውቂያ መሄሪያ አይወቃም፤
ከሙን የሠረገላ መንኰራኵር አይሄድበትም፤
ጥቍር አዝሙድ በበትር፣
ከሙንም በዘንግ ይወቃል::
[28]እንጀራን ለመጋገር እህል ይፈጫል፤
ስለዚህ አንድ ሰው ለዘላለም እህል ሲወቃ
አይኖርም::
የመውቂያውን መንኰራኵር ቢያኼድበትም፣

[ገ] 15 ወይም፣ *ሐሰተኛ ጣዖታትን*
[ነ] 25 በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጕም በትክክል አይታወቅም::

28፥12 ዘፀ14፥14፤ ኢሱ1፥13፤ኢዮ11፥18፤ ኢሳ11፥10፤ ማቴ11፥28-29
28፥13 ቍ10፤ ኢሳ8፥15፤ማቴ21፥44
28፥14 2ዜና36፥16፤ ኢሳ1፥10
28፥15 ቍ2:18፤ መሳ9፥35፤ኢዮ5፥23፤ ኢሳ8፥7-8:19፤9፥15፤ 10፥26፤29፥6:15፤ 30፥28፤ኤር23፥24፤ ሕዝ11፥22
28፥16 መዝ118፥22፤ ኢሳ8፥14-15፤14፥32፤ 29፥22፤45፥17፤50፥7፤ 54፥4፤ኤር51፥26፤ ሐዋ2፥34-35:45፤ ዘካ12፥3፤ሐሥ4፥11፤ ሮሜ9፥33፤10፥11፤ 1ቆሮ3፥11፤ 2ጢሞ2፥19፤1ጴጥ2፥6
28፥17 ኢሱ10፥11፤ 2ነገ21፥13፤መዝ11፥7፤ ኢሳ5፥16፤8፥7
28፥18 ቍ15፤ ኢሳ5፥5፤7፥7፤63፥18፤ ዳን8፥13
28፥19 2ነገ24፥2፤ ኢዮ18፥11፤መዝ5፥3
28፥20 ኢሳ59፥6
28፥21 ዘፍ38፥29፤ ኢሱ9፥3፤1ዜና14፥11፤ ኢሳ10፥12፤65፥7፤ ሉቃ19፥41-44
28፥22 2ዜና36፥16፤ ኢሳ10፥22:23፤ ኤር29፥18፤ሰቆ2፥15፤ ሰፎ2፥15
28፥23 ኢሳ32፥9
28፥24 መክ3፥2
28፥25 ዘፀ9፥31:32፤ ሕዝ4፥9፤ማቴ23፥23
28፥26 መዝ94፥10
28፥27 ኢዮ41፥30፤ ኢሳ10፥5፤21፥10
28፥28 ኢሳ21፥10

28፥11 *በባዕድ ልሳን፤* የአሦራውያንን ቋንቋ ለማመልከት ነው::

28፥12 *የዕረፍት ቦታ፤* ሊታመኑበት የሚገባ እግዚአብሔር የሰጣቸውን ምድር ያመለክታል (26፥3፤30፥15፤40፥31፤ ኢሱ 1፥13 ይመ):: *መስማት አልፈለጉም፤* ከኤር 6፥16 ጋር ያነጻጽሩ::

28፥13 *ይሆንባቸዋል፤* ከነቢዩ የሚሰማው ቃል ባዶ ነው ስለሚሉ፣ የሚናገረው የእግዚአብሔር ቃል ለእነርሱ ባዶ ይሆንባቸዋል (6፥9-10 እና ማብ ይመ)::

28፥15:18 *ከሞት ጋር ቃል ኪዳን ገብተናል፤* ከሙታን ጋር መገናኘትን ወይም አምልኮተ ጣዖትን ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ ለመግለጽ የገባ ሊሆን ይችላል (8፥19 ይመ)፤ ሕዝቡ ከሚደርስባቸው አደጋ የተነሣ አንሞትም የሚል ስሜት ስለነበራቸው፣ ኢሳይያስ ጠንካራ ዘይቤያዊ አነጋገርን በመጠቀም በዚህ አቋማቸው ላይ ያፌዛል (ሆሴ 2፥18):: *ታላቅ መቅሠፍት፤* የአሦርንና የባቢሎንን ሰራዊት የሚያመለክት ተለዋጭ ዘይቤ ነው፤ 8፥7፤ 10፥26 ይመ::

28፥16 *ድንጋይ፤* እግዚአብሔር ነው (8፥14፤ 17፥10 እና ማብ ይመ):: *የማዕዘን ድንጋይ፤* ከመዝ 118፥22 ጋር ያነጻጽሩ:: *ለጽኑ መሠረት፤* 1ቆሮ 3፥11 ይመ፤ ከ1ጴጥ 2፥4-7 ጋር ያነጻጽሩ::

28፥17 *የመለኪያ ገመድ … ቱንቢ፤* መለኪያዎቹና መፈተኛዎቹ እግዚአብሔር የሚፈጽማቸው የፍትሕና የጽድቅ ሥራዎች ይሆናሉ:: *የበረዶ ዝናብ፤* ቍ 2፤ 30፥30፤ 32፥19 ይመ::

28፥20 *አጭር ነው፤ … ጠባብ ነው፤* በወታደራዊም ሆነ በመንፈሳዊ ሕይወት እስራኤላውያን አልተደራጁም ነበር::

28፥21 *በፐራሲም ተራራ፤* እግዚአብሔር ፍልስጥኤማውያንን የመታበት ስፍራ ነው (2ሳሙ 5፥20 ይመ):: *በገባዖን ሸለቆ፤* አሞራውያንን ለማጥፋት እግዚአብሔር የበረዶ ድንጋይ ያወረደበት ስፍራ ነው (ኢሱ 10፥10-12):: *ድንቅ ሥራውን … እንግዳ የሆነ ተግባሩን፤* በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር እስራኤልን ይወጋል ማለት ነው::

28፥22 *ለማጥፋት ያወጀውን ዐዋጅ፤* 10፥22-23 እና የ10፥22 ማብ ይመ::

*28፥23-29፤* የጥበብ ቅኔ ሲሆን፣ በሁለት አንጓዎች ተከፍሎ እያንዳንዱ ስንኝ የእግዚአብሔርን ጥበብ ከፍ ከፍ በሚያደርግ ቃል ይጠቃለላል:: በአጠቃላይ ሐሳቡ፣ በተለይ “መውቃት” የሚለው ቃልም ጉልቶ መጠቀሱ ምንም እንኳ እግዚአብሔር እስራኤልን መቅጣት ቢኖርበትም፣ ቅጣቱ እንደ ገበሬ መከር ሁሉ በጊዜ ተለይቶ የሚታወቅና የሚለካ መሆኑን ያመለክታል፤ 27፥12 እና ማብ ይመ::

28፥25 *ከሙን፤* የምግብ ማጣፈጫ ቅመም:: *አጃ፤* የስንዴ ዐይነት ነው (የዘፀ 9፥32 ማብ ይመ)::

28፥27 *በትር፤* 10፥5 እና ማብ ይመ::

ፈረሶቹ አይደፈጥጡትም።
[29]ይህ ሁሉ የሚሆነው በምክሩ ድንቅ በጥበቡ
ታላቅ ከሆነው፣
ከሰራዊት ጌታ ከእግዚአብሔር ዘንድ ነው።

**ወዮ ለዳዊት ከተማ**

**29** ዳዊት የሰፈረብሽ ከተማ፣
አርኤል፣ አርኤል ወዮልሽ!
ዓመት በዓመት ላይ ጨምሪ፣
ዐውደ ዓመትሽም ይቀጥል።
[2]ነገር ግን አርኤልን[T] እከባለሁ፤
ታለቅሳለች፤ ዋይ ዋይ ትላለች፤
ለእኔም እንደ መሠዊያ ስፍራ ትሆንልኛለች።
[3]በዙሪያሽ እሰፍራለሁ፤
በቅጥር እከብሻለሁ፤
የከበባ ዐምባም ሠርቼ አስጨንቅሻለሁ።
[4]ወደ ታች ትወርጃለሽ፤ ከምድርም በታች
ትናገሪያለሽ፤
ንግግርሽ ከትቢያ እየተጕተመተመ
ይወጣል፤
ድምፅሽ እንደ መናፍስት ድምፅ ከመሬት
ወደ ላይ ይመጣል፤
ንግግርሽ ከትቢያ ያንሾካሹካል።
[5]ነገር ግን ብዙ ጠላቶችሽ እንደ ትቢያ ብናኝ፣
መንጋ ጨካኞችም በነፋስ እንደሚነዳ ገለባ
ይሆናሉ።
ድንገት ሳይታሰብም፣
[6]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
በነጐድጓድ፣ በምድር መናወጥና በታላቅ
ድምፅ፣
በዐውሎ ነፋስና በኀይለኛ ሞገድ ፈጽሞ
በሚባላም የእሳት ነበልባል ይመጣል።
[7]አርኤልን የሚወጋ የአሕዛብ ሁሉ መንጋ፣
በእርሷና በምሽጓ ላይ አደጋ የሚጥልና
የሚከባት፣
እንደ ሕልም
በሌሊትም እንደሚታይ ራእይ ይሆናል።
[8]የተራበ ሰው በሕልሙ ሲበላ ዐድሮ፣
ነገር ግን ሲነቃ ራቡ እንዳልለቀቀው፣
የጠማውም ሰው በሕልሙ ሲጠጣ ዐድሮ፣
ነገር ግን ሲነቃ እንደ ዛለና ጥማቱም
እንዳልተወው፣
የጽዮንን ተራራ የሚወጋ፣
የአሕዛብ መንጋ ሁሉ እንዲሁ ይሆናል።
[9]ነሁሉሉ፤ ተደነቁም፤
ተጨፈኑ፤ እስከ ወዲያኛውም ታውራችሁ
ቅሩ፤
በወይን ጠጅ አይሁን እንጂ ስከሩ፤
በሚያሰክር መጠጥ አይሁን እንጂ
ተንገዳገዱ።
[10]እግዚአብሔር ከባድ እንቅልፍ ጥሎባችኋል፤
ዐይኖቻችሁን፣ ነቢያትን ጨፍኖባችኋል፤
ራሶቻችሁን፣ ባለ ራእዮችን ሸፍኖባችኋል።

[11]ይህ ሁሉ ራእይ በጥቅልል መጽሐፍ ውስጥ እንደ ታሸገ ቃል ሆኖባችኋል። ጥቅልሉንም መጽሐፍ ማንበብ ለሚችል ሰው፣ "እባክህ አንብልን" ብላችሁ ብትሰጡት፣ "ታሽጓልና አልችልም" ይላችኋል። [12]ደግሞም ጥቅልሉን መጽሐፍ ማንበብ ለማይችል ሰው፣ "እባክህን አንብልን" ብላችሁ ብትሰጡ፣ "ማንበብ አል ችልም" ይላችኋል።

[13]እግዚአብሐር እንዲህ ይላል፤
"ይህ ሕዝብ በአፉ ወደ እኔ ይቀርባል፤
በከንፈሩም ያከብረኛል፤
ልቡ ግን ከእኔ የራቀ ነው፤
የሚያመልከኝም፣
ሰው ባስተማረው ሰው ሠራሽ ሥርዐት ብቻ
ነው[A]።
[14]ስለዚህ ይህን ሕዝብ በድንቅ ላይ ድንቅ
ነገር እያደረግሁ፣
ዳግመኛ አስገርመዋለሁ፤
የጥበበኞች ጥበብ ይጠፋል፤
የአስተዋዮችም ማስተዋል ይበናል።"

28፥29 መዝ92፥5፤ ኢሳ9፥6፤ሮሜ11፥33
29፥1 ቍ2፡7፤ 2ሳሙ5፥7፤ኢሳ1፥14፤ 22፥12-13፤28፥1
29፥2 ቍ11 ኢሳ3፥26፤ሰቆ2፥5፤ ሕዝ43፥15
29፥3 2ነገ25፥1፤ ሉቃ19፥43-44
29፥4 ዘሌ19፥31፤ ኢሳ8፥19፤26፥16፤ 47፥1፤52፥2
29፥5 ዘዳ9፥21፤ መዝ55፥15፤78፥39፤ 103፥15፤ኢሳ2፥22፤ 13፥11፤17፥13፡14፤ 37፥27፤40፥6፤51፥12፤ 1ተሰ5፥3
29፥6 ዘፀ19፥16፤ ዘሌ10፥2፤መዝ50፥3፤ 55፥8፤83፥13-15፤ ኢሳ26፥21፤28፥15፤ ዘካ14፥1-5፤ማቴ24፥7፤ ማር13፥8፤ሉቃ21፥11፤ ራእ6፥12፤11፥19
29፥7 ቍ1፤ ኢዮ20፥8፤ሚክ4፥11-12፤ ዘካ12፥9
29፥8 ቍ5፡7፤ መዝ73፥20፤ኢሳ17፥12-14፤41፥11፡15፤ 54፥17፤ኤር30፥16፤ ዘካ12፥3
29፥9 ቍ14፤ ዘሌ10፥9፤መዝ60፥3፤ ኢሳ3፥12፤6፥10፤ 28፥1፤51፥17፡21-22፤ 63፥6፤ኤር4፥9፤ 13፥13፤25፥27፤ዕን1፥5
29፥10 መሳ4፥21፤ 1ሳሙ9፥9፤ መዝ69፥23፤ ኢሳ6፥9-10፤44፥18፤ ዮና1፥5፤ሚክ3፥6፤ ሮሜ11፥8፤2ተሰ2፥9-11
29፥11 ኢሳ8፥16፤ 28፥7፤ዳን8፥26፤ 12፥9፤ማቴ13፥11፤ ራእ5፥1-2
29፥13 መዝ50፥16፤ 119፥70፤ኢሳ58፥2፤ ኤር12፥2፤14፥11፤ ሕዝ33፥31፤ሐጌ1፥2፤ 2፥14፤ማቴ15፥8-9፤ ማር7፥6-7፤ቈላ2፥22

29፥14 ኢዮ5፥13፤ 10፥16፤ኢሳ6፥9-10፤ኤር8፥9፤49፥7፤1ቆሮ1፥19

[T]2 በዕብራይስጡ፣ *የመሠዊያ መሬት* የሚለው ቃል ድምፀት፣ *አርኤል* ከሚለው ቃል ጋር አንድ ዐይነት ነው።
[A]13 ዕብራይስጡ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ግን፣ *በከንቱ ያመልኩኛል፤ ትምህርታቸው ሰው ያስተማረው ሰው ሠራሽ ሥርዐት ብቻ ነው* ይላል።

28፥29 *በምክሩ ድንቅ፤* 9፥6 እና ማብ ይመ።

29፥1፡2፡7 *አርኤል፤* ኢየሩሳሌም ናት። ውጊያና ደም መፋሰስ ኢየሩሳሌምን፣ "የመሠዊያ ምድጃ ያደርጋታል" የሚል ትርጕም ይሰጣል፤ ተመሳሳይ የዕብራይስጥ ቃል በሕዝ 43፥15-16 ላይ ተጠቅሶአል።

29፥1 *ወዮልሽ፤* የ28፥1 ማብ ይመ። *ዳዊት የሰፈረብሽ ከተማ፤* 2ሳሙ 5፥6-9 ይመ። *ዐውደ ዓመትሽም፤* 1፥13-14 እና የ1፥14 ማብ ይመ።

29፥3 *በቅጥር፤* የከተማዪቱን ተከላካዮች በተመሳሳይ አቋም ለመውጋት እንዲያስችላቸው አጥቂዎች ከከተማዪቱ ቅጥር በማስጠጋት የግንብ ማማ ሠርተው ነበር።

29፥4፤ *ያንሾካሹካል፤* በ8፥19ላይ ስለ ሙታን ጠሪዎችና ስለ አስማተኞች ተመልክቶአል፤ ከሙታን ጋር ስላለው ቃል ኪዳን ይሁዳ ከሞት መጋረጃ ጀርባ ባለው ስፍራ እንዳለ ሰው ሆኖ ይናገራል (28፥15፡18 ይመ)።

*29፥5-8፤* በእግዚአብሔር ጊዜ፣ ኢየሩሳሌምን የሚያጠፉ ራሳቸውም ይጠፋሉ (10፥5-9፤ 27፥1 ይመ)። 701 ዓ.ቅ.ክ ላይ የተደመሰሰው የአሦር ሰራዊት ለጠላት በድንገት መደምሰስ ጥሩ ምሳሌ ነው (10፥16 እና ማብ ይመ)።

29፥5 *ገለባ፤* 17፥13 እና የመዝ 1፥4 ማብ ይመ።

29፥6 *በነጐድጓድ፣ በምድር መናወጥና ... በዐውሎ ነፋስና በኀይለኛ ሞገድ፤* መሳ 5፥4-5፤ መዝ 18፥7-15፤ ዕን 3፥3-7፤ 28፥2፤ መዝ 83፥13-15 እና ማብ ይመ።

*29፥9-14፤* ኢሳይያስ እስራኤላውያን ያሉብትን መንፈሳዊ ሁኔታ በማመልከት ስለሚመጣው የእግዚአብሔር ፍርድ እንደ ገና ማስጠንቀቂያ ሰጥቶአል።

29፥9 *ታውራችሁ ቅሩ ... ስከሩ፤* በመንፈሳዊ ረገድ እጅግ ዝቅተኛ ደረጃ ላይ መሆናቸውን ለማመልከት ነው (6፥10 እና ማብ ይመ፤ ከ28፥1፡7 ጋር ያነጻጽሩ)።

*29፥10፤* በከፊል በሮሜ 11፥8ላይ ተጠቅሶአል። *ባለ ራእዮችን፤* 1ሳሙ 9፥9እና ማብ፤ 2ነገ 17፥13 ይመ።

29፥11 *ራእይ፤* 1፥1 እና ማብ ይመ። *አልችልም፤* የእግዚ አብሔር ቃል ለተማሩት እንኳ የተዘጋ ሊሆን ይችላል።

*29፥13፤* ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የፈሪሳውያንን ግብዝነት በማቴ 15፥8-9 ለማሳየት ጠቅሶታል። *ይህ ሕዝብ፤* "ሕዝቤ" አላለም (ከ8፥6፡11-12፤ ከኤር 14፥10-11፤ ከሐጌ 1፥2 ጋር ያነጻጽሩ)።

*29፥14፤* በከፊል በ1ቆሮ 1፥19 ተጠቅሶአል። *በድንቅ ላይ ድንቅ፤* እስራኤል ከግብፅ በወጡ ጊዜ ድንቅ ያሳያቸው (ዘፀ 15፥11፤ መዝ 78፥12 ይመ)፣ አሁንም በፍርዱ ድንቅ ያሳያቸዋል ማለት ነው። *የጥበበኞች ጥበብ ይጠፋል፤* ከ44፥25፤ ኤር 8፥9

[15]ሐሳባቸውን *ከእግዚአብሔር* ለመደበቅ፣
ወደ ጥልቅ ጕድጓድ ለሚወርዱ
ሥራቸውንም በጨለማ ለሚያከናውኑ፣
"ማን ያየናል? ማንስ ያውቅብናል" ለሚሉ
ወዮላቸው!
[16]እናንተ ነገሮችን ትገለብጣላችሁ!
ሸክላ ሠሪውን እንደ ሸክላ ትመለከታላችሁ፤
ለመሆኑ፣ ተሠሪ ሠሪውን፣
"እርሱ አልሠራኝም" ይለዋልን?
ሸክላ የሠራውን፣
"እርሱ ምንም አያውቅም" ይለዋልን?
[17]ሊባኖስ ወደ ለም ዕርሻነት ለመለወጥ፣
ለም የሆነውም መሬት ወደ ዱርነት
ለመለወጥ ጥቂት ጊዜ አልቀረውምን?
[18]በዚያ ጊዜ ደንቈሮ የጥቅልሉን መጽሐፍ
ቃል ይሰማል፤
የዕይነ ስውሩም ዐይኖች
ከጭጋግና ከጨለማ ተላቀው ያያሉ።
[19]ትሑታን *በእግዚአብሔር*፣
ምስኪኖችም በእስራኤል ቅዱስ እንደ
ገና ሐሤት ያደርጋሉ።
[20]ጨካኞች እንዳልነበሩ ይሆናሉ፤
ፌዘኞችም በነው ይጠፋሉ፤
ለክፋት ያደፈጡ ሁሉ ይወገዳሉ።
[21]ሰውን በነገር በደለኛ የሚያደርጉ፣
በተከሳሽ ላይ ወጥመድ የሚዘረጉ፣
በሐሰት ምስክር ፍትሕን ከንጹሓን የሚቀሙ
ይቈረጣሉ።
[22]ስለዚህ አብርሃምን የተቤዠው *እግዚአብሔር*
ለያዕቆብ ቤት እንዲህ ይላል፤
"ያዕቆብ ከእንግዲህ ወዲያ አያፍርም፤
ፊቱም ከእንግዲህ አይለዋወጥም።
[23]በመካከላቸው የእጄ ሥራ የሆኑ፣
ልጆቻቸውን ሲያዩ፣
ስሜን ይቀድሳሉ፤
የያዕቆብን ቅዱስ ቅድስና ያውቃሉ፤
በእስራኤልም አምላክ ፊት በፍርሀት
ይቆማሉ።
[24]በመንፈስ የሳቱ ያስተውላሉ፤
የሚያጕረመርሙም ምክር ይቀበላሉ።"

## ወዮ ለእምቢተኛ ሕዝብ

**30** "ለዐመፀኞች ልጆች ወዮላቸው"
ይላል *እግዚአብሔር*፤
"የእኔ ያልሆነውን ሐሳብ ይከተላሉ፤
ከመንፈሴ ያልሆነውን ቃል ኪዳን ያደርጋሉ፤
በኀጢአት ላይ ኀጢአት ይጨምራሉ።
[2]እኔን ሳይጠይቁ፣
ወደ ግብፅ ይወርዳሉ፤
የፈርዖንን ከለላ፣
የግብፅንም ጥላ ለመጠጊያነት ይፈልጋሉ።
[3]ነገር ግን የፈርዖን ከለላ ውርደት ይሆንባችኋል፤
የግብፅም ጥላ ኀፍረት ያመጣባችኋል።
[4]ምንም እንኳ ሹሞች በጣኔዎስ ቢኖሩቸውም፣
መልእክተኞቻቸው ሓኔስ ቢደርሱም፣
[5]ውርደትና ኀፍረት ብቻ እንጂ
ርዳታም ሆነ ረብ በማያስገኙላቸው
ምንም ጥቅም በማይሰጧቸው ሰዎች ምክንያት
ሁሉም ለኀፍረት ይዳረጋሉ።"

29፥15 ዘፍ3፥8፤ 2ነገ21፥16፤ኢዮ8፥3፤ 22፥13፤መዝ10፥11-13፤ 94፥7፤ኢሳ28፥15፤ 47፥10፤57፥12፤ ሕዝ8፥12፤9፥9
29፥16 ዘፍ2፥7፤ ኢዮ9፥12፤10፥9፤ ኢሳ10፥15፤45፥9፤ 64፥8፤ኤር18፥6፤ ሮሜ9፥20-21
29፥17 መዝ84፥6፤ 107፥33፤ኢሳ2፥13፤ 10፥25፤32፥15
29፥18 መዝ107፥14፤ 146፥8፤ኢሳ28፥5፤ 32፥3፤ማቴ11፥5፤ ማር7፥37፤ሉቃ7፥22
29፥19 ቍ23፤ መዝ25፥9፤37፥11፤ 72፥4፤ኢሳ1፥4፤3፥15፤ 5፥19፤12፥6፤14፥30፤ 30፥11፤61፥1፤ ማቴ5፥5፤11፥5፡29፤ ሉቃ7፥22፤ያዕ1፥9፤ 2፥5
29፥20 2ዜና36፥16፤ ኢዮ15፥35፤መዝ7፥14፤ ኢሳ9፥4፤13፥11፤ 28፥22፤32፥7፤33፥11፤ 34፥12፤59፥4፤ ሕዝ11፥2፤ሚክ2፥1፤ ናሆ1፥11
29፥21 ምሳ21፥28፤ ኢሳ5፥23፤32፥7፤ አሞ5፥10፡15፤ዕን1፥4
29፥22 ዘፍ17፥16፤ ዘፀ6፥6፤መዝ22፥5፤ 25፥3፤ኢሳ28፥16፤ 41፥8፤49፥23፤51፥2፤ 61፥7፤63፥16፤ ኤር30፥6፡10፤ ኢል2፥6፡21፡26፤ ናሆ2፥10፤ሶፎ3፥11
29፥23 ቍ19፤ መዝ8፥6፤ኢሳ5፥19፤ 19፥25፤49፥20-26፤ 53፥10፤54፥1-3፤ማቴ6፥9
29፥24 መዝ95፥10፤ ምሳ12፥8፤ ኢሳ1፥3፤28፥7፤30፥21፤32፥4፤ 41፥20፤42፥16፤60፥16፤ዕብ5፥2
30፥1 ዘዳ21፥18፤2ነገ17፥4፤ኢሳ1፥2፤8፥12፤28፥1
30፥2 ዘፍ25፥22፤ዘኍ27፥21፤2ነገ25፥26፤ኢሳ4፥6፤31፥1፤ 36፥6፡9፤ኤር2፥18፡36፤42፥14፤ሕዝ17፥15፤29፥16
30፥3 ቍ5፤ መሳ9፥8-15፤መዝ44፥13፤ኢሳ20፥4-5፤36፥6
30፥4 ዘኍ13፥22 30፥5 ቍ3፡7፤ 2ነገ18፥21፤ መዝ108፥12፤ ኢሳ20፥5፤31፥1፤36፥6፤ኤር37፥3-5፤ሕዝ17፥15

ጋር ያነጻጽሩ።

29፥15 *ሐሳባቸውን፤* ምናልባት በአካዝና በአሦር መካከል ወይም በሕዝቅያስና በግብፅ መካከል የነበረውን ስምምነት የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (30፥1-2 ይመ)። *ማን ያየናል?* የመዝ 10፥11 ማብ ይመ። *ወዮላቸው፤* እዚህ ላይ ወዮታው እንደ ገና ይጀምራል (የ28፥1-35፥10 ማብ ይመ)።

*29፥16፤* በከፊል በሮሜ 9፥20 ላይ ተጠቅሶአል፤ በዘፍ 2፥7 ላይ ከተጠቀሰው ከአዳም መፈጠር ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም ኢሳ 10፥15 ያነጻጽሩ።

*29፥17-24፤* በ28፥5-8 እንደ ተገለጸው ወደ ድኅት ፍሬ ሐሳብ ድንገት ዘወር የተባለበት ክፍል ነው።

29፥17 *ሊባኖስ፤* ምናልባት አሦርን የሚያመለክት ነው (10፥34 ይመ)። የሊባኖስ ደን ተወዳዳሪ የለውም (2፥13 ይመ)፤ ስለዚህ "ለም እርሻ" ዝቅተኛ ግምት ይሰጠው ነበር ማለት ነው (32፥15 ይመ)።

29፥18 *በዚያ ጊዜ፤* የ10፥20፡27፤ 26፥1 ማብ ይመ። አሦር የሚደመሰስበት ቀን ካለፈ በኋላ፣ እስራኤል ተመልሳ ትቋቋ ማለች። *ደንቈሮ ... ይሰማል የዐይነ ስውሩም ዐይኖች ... ያያሉ፤* በ35፥5 ላይ ከተገለጸው ከመሲሑ ዘመን ጋር የተያያዘ ነው።

29፥19 *ምስኪኖችም፤* 11፥4 ይመ። *በእስራኤል ቅዱስ፤* የ1፥4 ማብ ይመ።

29፥20 *ጨካኞች፤* ቍ 21 ይመ። *ፌዘኞችም፤* ከ28፥14፡22 ጋር ያነጻጽሩ።

29፥21 *ፍትሕን ... የሚቀሙ፤* 1፥17፤ 9፥17 እና ማብ ይመ፤ 10፥2፤ አሞ5፥10፡12 ይመ።

29፥22 *የተቤዠውን፤* ይህ አገላለጽ የሚያመለክተው ከግብፅ የወጡትን እስራኤላውያን ነው (ዘፀ 6፥6፤ 15፥13 ይመ) ከ43፥1፡3፡14 ጋር ያነጻጽሩ። ይሁን እንጂ አብርሃምም እንደዚሁ ከጣዖት አምላኪው ዓለም ተለይቶ ነጻ ወጥቶአል (ዘፍ 12፥1፤ ኢያ 24፥2-3፡ 14-15 ይመ)። *አያፍርም፤* ከ45፥17፤ 50፥7፤ 54፥4 ጋር ያነጻጽሩ። *ፊቱም ... አይለዋወጥም፤* ጠላትን ከመፍራት የተነሣ ማለት ነው።

29፥23 *ልጆቻቸውን ሲያዩ፤* ከ49፥20-21፤ 54፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ። ከምርኮ መልሶ እንደ ገና መቋቋምን ሲገልጽ ነው፤ 53፥10 ይመ። *የእጄ ሥራ የሆኑ፣ ልጆቻቸውን፤* 45፥11 ይመ፤ ከኤፌ 2፥10 ጋር ያነጻጽሩ። *ቅድስና ያውቃሉ ... በፍርሀት ይቆማሉ፤* 8፥13 ይመ። በኢሳይያስ ዘመን የነበሩ ሰዎች እግዚአብሔርን ይህን ያህል አያከብሩትም ነበር። *የያዕቆብን ቅዱስ፤* ከቍ 19 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ1፥4 ማብ ይመ።

29፥24 *በመንፈስ የሳቱ፤* 19፥14 ይመ። *ያስተውላሉ፤* ከ1፥3 ጋር ያወዳድሩ።

30፥1 *ለዐመፀኞች ልጆች፤* 1፥2 እና ማብ ይመ። *ወዮላቸው፤* የ28፥1-35፥10 ማብ ይመ። *የእኔ ያልሆነውን ሐሳብ ይከተላሉ፤* 29፥15 እና ማብ ይመ። *ከመንፈሴ፤* በነቢዩ በኩል የሚናገረው የእግዚአብሔር መንፈስ ነው። *ቃል ኪዳን ያደርጋሉ፤* በ715 ዓ.ቅ.ክ ሻባኮ በግብፅ ንግሥ ፈርዖን ከተባለ በኋላ፣ እንደ ሶርያና ከነዓን ያሉ ትንንሽ መንግሥታት ከአሦር የሚመጣባቸውን ጥቃት ለመከላከል ከግብፅ ጋር ስምምነት አደረጉ፤ ይሁዳም ተባበራቸው (20፥5 እና ማብ ይመ)።

*30፥2፤* ይህን ያደረገው ሕዝቅያስ ነው (2ነገ 18፥21 ይመ)። *ጥላ፤* ርዳታ የተጠየቀውን ንጉሥ በተለዋጭ ዘይቤ ለመግለጽ የገባ ቃል ነው (መሳ 9፥15፤ ሰቆ 4፥20 ይመ)። እግዚአብሔር የእስራኤል "ጥላ" ነው (ከ49፥2፤ 51፥16 ጋር ያነጻጽሩ፤ መዝ 91፥1፤ 121፥5 ይመ)።

30፥3፡5 *ውርደት ... ኀፍረት፤* ከ20፥4-5 ጋር ያነጻጽሩ፤ መሳ 9፥14-15 እና ማብ ይመ።

30፥4 *በጣኔዎስ፤* እስራኤላውያን ጥንት በባርነት ቀንበር ሥር ሳሉ የነበሩበትን ቦታ በሽሙጥ ለመግለጽ የገባ ቃል ነው (19፥11 እና ማብ ይመ)። *ሓኔስ፤* ምናልባት ከካይሮ በስተ ደቡብ 80 ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ የምትገኝ ሄራክሊኦፖሊስ ማግና ወይም በዐባይ ወንዝ መፋሰሻ ላይ

[6]በኔጌብ ስላሉት እንስሳት የተነገረ ንግር፤
መልእክተኞች ሀብታቸውን በአህያ፣
ውድ ዕቃዎቻቸውን በግመል ጭነው፣
ተባዕትና እንስት አንበሶች፣
መርዘኛና ተወርዋሪ እባቦች በሚኖሩበት፣
መከራና ጭንቅ ባለበት ምድር ዐልፈው፣
ወደማይጠቅማቸው ወደዚያ ሕዝብ፣
[7]ርዳታዋም ፈጽሞ ዋጋ ቢስ ወደ ሆነው ወደ ግብፅ ይሄዳሉ።
ስለዚህ ስሟን፣
ረዓብ፣ ምንም የማትጠቅም ብዬ እጠራታለሁ።

[8]አሁንም ሂድ፤ በሰሌዳ ላይ ጻፍላቸው፤
በጥቅልል መጽሐፍ ላይ ክተብላቸው፤
ለሚመጡትም ዘመናት፣
ለዘላለም ምስክር ይሆናል፤
[9]እነዚህም የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ለመስማት የማይፈልጉ፣
ዐመፀኛ ሕዝቦችና አታላይ ልጆች ናቸው።
[10]ባለ ራእዮችን፣
"ከእንግዲህ ራእይን አትዩ" ይላሉ፤
ነቢያትንም እንዲህ ይላሉ፤
'እውነተኛውን ትንቢት ከእንግዲህ አትንገሩን፤
ደስ የሚያሰኘውን ንገሩን፤
የሚያማልለውን ተንብዩልን።
[11]ከዚህ መንገድ ፈቀቅ በሉ፤
ከጐዳናውም ራቁ፤
ከእስራኤል ቅዱስ ጋር
ፊት ለፊት አታጋጥሙን።'"

[12]ስለዚህ፣ የእስራኤል ቅዱስ እንዲህ ይላል፤
"ይህን ቃል ስላቃለላችሁ፣
ግፍን ስለታመናችሁ፣
ማታለልን ስለ ተደገፋችሁ፣
[13]ስለዚህ ይህ ኀጢአት፣
ተሰንጥቆ ሊወድቅ እንደ ደረሰ፣
ሳይታሰብ ድንገት እንደሚወድቅ ረጅም ቅጥር ይሆንባችኋል።
[14]ከሰብርባሪዎቹም መካከል፣
ለፍም መጫሪያ፣
ለውሃ መጥለቂያ ገል እስከማይገኝ ድረስ፣
ምንም ሳይቀር ክፉኛ እንደሚንኰታኰት፣
የሸክላ ዕቃ ይደቃል።"

[15]የእስራኤል ቅዱስ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

"በመመለስና በማረፍ ትድናላችሁ፤
በጸጥታና በመታመን ትበረታላችሁ፤
እናንተ ግን ይህን አላደረጋችሁም፤
[16]ደግሞም 'አይሆንም፣ በፈረስ እንሸሻለን'
አላችሁ፤
ስለዚህ ትሸሻላችሁ።
ደግሞም፣ 'በፈጣን ፈረስ እናመልጣለን'
አላችሁ፤
ስለዚህ አሳዳጆቻችሁም ፈጣን ይሆናሉ።
[17]በተራራ ዐናት ላይ እንደ ተተከለ ሰንደቅ ዐላማ፣
በኰረብታም ላይ እንደ ቆመ ምልክት፣
ሆናችሁ እስክትቀሩ ድረስ
በአንድ ሰው ዛቻ፣
ሺህ ሰው ይሸሻል፤
በአምስት ሰው፣
ሁላችሁ ትሸሻላችሁ።"
[18]እግዚአብሔር ግን ምሕረት ሊያደርግላችሁ ይታገሣል፤
ርኅራኄም ሊያሳያችሁ ይነሣል።
እግዚአብሔር የፍትሕ አምላክ ነውና፣
እርሱን በመተማመን የሚጠባበቁት
የተባረኩ ናቸው።

[19]በኢየሩሳሌም የምትኖሩ የጽዮን ሕዝብ ሆይ፤ ከእንግዲህ ወዲህ አታለቅሱም። ለርዳታ ወደ እርሱ ስትጮኹ እንዴት ምሕረት አያደርግላችሁም! ጩኸትህን እንደ ሰማም ፈጥኖ ይመልስልሃል። [20]ጌታ የጭንቀት እንጀራና የመከራ ውሃ ቢሰጥህም፣ አስተማሪህ ከእንግዲህ አይሰወርብህም፤ ዐይኖችህም አስተማሪህን ያያሉ። [21]ወደ ቀኝም ሆነ ወደ ግራ ዘወር ብትል ጆሮህ ከኋላህ፣ "መንገዱ ይህ ነው፤ በእርሱ

30፥6 ዘፍ42፥26፤ ዘፀ1፥13፤5፥10:21፤ ዘዳ8፥15፤መሳ1፥9፤ 1ሳሙ25፥18፤ ኢሳ5፥29:30፤8፥22፤ 13፥1፤15፥7፤35፥9፤ ኤር11፥4 30፥7 2ነገ18፥21፤ ኢዮ9፥13፤ኤር2፥36 30፥8 ዘፀ17፥14፤ ዘዳ27፥8፤ኢሱ24፥26-27፤ኢሳ8፥1፤ ኤር25፥13፤30፥2፤ 36፥28፤ዕን2፥2 30፥9 መዝ78፥8፤ ኢሳ1፥2:10፤28፥15፤ 59፥3-4፤ሕዝ2፥6 30፥10 1ሳሙ9፥9፤ 1ነገ22፥8፤ኤር4፥10፤ 11፥21፤23፥26፤25፥9፤ 26፥9፤32፥3፤36፥29፤ ሕዝ13፥7፤አሞ7፥13፤ ሮሜ16፥18፤ 2ጢሞ4፥3-4 30፥11 ቍ21፤ ኢዮ21፥14፤ምሳ3፥6፤ ኢሳ29፥19፤35፥8-9፤ 48፥17 30፥12 ቍ15፤ መዝ10፥7፤12፥5፤ ኢሳ5፥7:19:24፤31፥1 30፥13 1ነገ20፥30፤ ነህ2፥17፤መዝ62፥3፤ 80፥12፤ኢሳ17፥14 30፥14 መዝ2፥9 30፥15 ቍ12፤ ዘፀ14፥14፤ኢሱ1፥13፤ 2ዜና20፥12፤ኢሳ8፥6፤ 32፥17፤42፥24፤ 57፥17፤ኤር7፥20፤ ሕዝ3፥11 30፥16 ዘዳ17፥16፤ 1ነገ10፥28-29፤ መዝ20፥7፤ ኢሳ31፥1:3፤ 36፥8፤ኤር46፥6 30፥17 ዘሌ26፥8: 36፤ዘዳ28፥25፤ 2ነገ7፥7፤መዝ20፥5፤ ኢሳ1፥8 30፥18 ዘፍ43፥31፤ መዝ11፥7፤ 27፥14፤ 78፥38፤ኢሳ5፥16፤ 25፥9፤33፥2፤40፥31፤ 42፥14፤48፥9፤64፥4፤ ሰቆ3፥25፤ዳን12፥12፤ ዮና3፥10፤2ጴጥ3፥9:15 30፥19 ኢዮ22፥27፤24፥12፤መዝ50፥15፤ 86፥7፤ኢሳ25፥8፤41፥17፤ 58፥9፤60፥20፤61፥3፤65፥24፤ዘካ13፥9፤ ማቴ7፥7-11 30፥20 1ነገ22፥27፤ መዝ74፥9፤ኢሳ28፥9፤ አሞ8፥11 30፥21 ቍ11፤ኢዮ33፥11፤ኢሳ29፥24

ከጣኔዎስ አጠገብ ያለች ከተማ ሳትሆን አትቀርም።

30፥6 *ኔጌብ፤* በፍልስጥኤም ምድር በደቡብ ክፍል የሚገኝ ጭው ያለ ምድረ በዳ (ዘፍ 12፥9 እና ማብ ይመ፤ ከመሳ 1፥9 ጋር ያነጻጽሩ)። *ንግር፤* 13፥1 እና ማብ ይመ። *መከራና ጭንቅ፤* በጠረፍ በኩል ያለውን ዋና መንገድ አሦራውያን ስለ ተቈጣጠሩት፣ በስተ ጀርባ ያለውን መንገድ መጠቀም የግድ ሳያስፈልግ አልቀረም ነበር (ዘዳ 8፥15፤ መሳ 5፥6 ይመ)። *ተወርዋሪ እባቦች፤* 14፥29 ይመ።

30፥7 *ረዓብ፤* የባሕር አውሬ እንደ ሆነ በአፈ ታሪክ ይነገራል። ግብፅን ለመግለጥ በምሳሌ የገባ ቃል ነው። ትርጕሙም፣ "ማዕበል" እንዲሁም፣ "እብሪት" ማለት ነው።

30፥8 *ጻፍላቸው፤* የሚጻፈው፣ "ምንም ማድረግ የማይችለው ረዓብ" የሚል ነው።

30፥9 *ዐመፀኛ ሕዝቦች፤* ቍ 1 ይመ፤ 1፥2 እና ማብ ይመ።

30፥10 *ባለ ራእዮችን፤* 1ሳሙ 9፥9 እና ማብ ይመ፤ 2ነገ 17፥13 ይመ። *ከእንግዲህ ራእይን አትዩ፤* ከአሞ 2፥12 ጋር ያነጻጽሩ። *ደስ የሚያሰኘውን ንገሩን፤* የሐሰት ነቢያት እንደሚያደርጉት (1ነገ 22፥13፤ ኤር 6፥14፤ 8፥11፤ 23፥17:26፤

30፥11-12:15 *የእስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4 እና ማብ ይመ።

30፥12 *ግፍን፤* በተለይ በአገራቸው የውስጥ አስተዳደር ጕዳይ የሚታይ ነው (1፥15-17:23፤ 5፥7፤ 29፥21፤ 58፥3-4፤ 59፥3:6-8:13)። *ማታለል፤* የውጭ አስተዳደር ጕዳያቸውን ይመለከታል (ቍ 1-2፤ 29፥15 ይመ)።

30፥13 *እንደሚወድቅ ረጅም ቅጥር፤* ስላማቸውንና ብልጽግናቸውን ለማስከበር እንደ ቅጥር የገነቡት ጭቈናንና ማታለልን ነበር (ቍ 12)፤ ነገር ግን ይንኰታኰታል።

*30፥15፤* 26፥3 ይመ። *በመመለስና በማረፍ፤* ለድነትና በሰላም ለመኖር እውነተኛው መንገድ ይህ ነው።

30፥16 *በፈረስ፤* መዝ 33፥17 ይመ።

30፥17 *ሺህ ሰው ይሸሻል፤* በዘዳ 32፥30 የተጠቀሰው ርግማን ፍጻሜ ነው። *ሰንደቅ ዐላማ ... ምልክት፤* 5፥26 እና ማብ ይመ (1፥8 እና ማብ ይመ)።

30፥18 *ምሕረት ሊያደርግላችሁ ይታገሣል፤* እግዚአብሔር፣ እስራኤልን አንድ ጊዜ ከቀጣ በኋላ እንደ ገና ይባርካቸዋል (ከ40፥2 ጋር ያነጻጽሩ)።

30፥19 *ከእንግዲህ ወዲህ አታለቅሱም፤* 25፥8 እና ማብ ይመ። እግዚአብሔር ስለ ወይኑ ቦታ (ስለ እስራኤል) ካደረበት ቅናት የተነሣ፣ እዚህ ላይ የተናገረው በ27፥2-6 ላይ ከተናገረው ጋር ይመሳሰላል።

30፥20 *የጭንቀት እንጀራና የመከራ ውሃ፤* የእስረኞችን ምግብ ያመለክታል (1ነገ 22፥27 ይመ)። *አስተማሪህ፤* እንደ ኢሳይያስ ያሉትን ነቢያት ያመለክታል።

30፥21 *መንገዱ ይህ ነው፤* ከቍ 10-11 የተገለጸውን ሐሳብ

ሂድ" የሚል ድምፅ ይሰማል:: [22]ከዚያም በብር የተለበጡትን ጣዖቶችህንና በወርቅ የተለበጹ ምስሎችህን ታዋርዳለህ፤ "ከዚህ ወግዱ!" ብለህም እንደ መርገም ጨርቅ ትጥላቸዋለህ:: [23]በምድርም ለዘራኸው ዘር ዝናብን ይሰጥሃል፤ ከመሬትም የሚገኘው ፍሬ ምርጥና የተትረፈረፈ ይሆናል:: በዚያን ቀን ከብቶችህ በትልቅ ሜዳ ላይ ይሰማራሉ:: [24]የዕርሻ በሬዎችና አህዮች በመንሽና በላይዳ የተለየውን ገፈራና ድርቆሽ ይበላሉ:: [25]በታላቁ የዕልቂት ቀን ምሽጎች ሲፈርሱ፣ በረጅም ተራራ ሁሉና ከፍ ባለውም ኰረብታ ሁሉ ላይ ወራጅ ወንዝ ይፈስሳል:: [26]*እግዚአብሔር* የሕዝቡን ስብራት ሲጠግን፣ ያቈሰለውንም ሲፈውስ፣ ጨረቃ እንደ ፀሓይ ታበራለች፤ የፀሓይም ብርሃን እንደ ሰባት ቀን ብርሃን ሰባት ዕጥፍ ይደምቃል::

[27]እነሆ፤ *የእግዚአብሔር* ስም፣
ከሚነድ ቍጣ፣ ጥቅጥቅ ካለና ከሚትጒለጒል
የጢስ ደመና ጋር ከሩቅ ይመጣል፤
ከንፈሮቹ ቍጣን የተሞሉ ናቸው፤
ምላሱም የሚባላ እሳት ነው::
[28]እስትንፋሱ እንደሚጠራርግ፣
እስከ ዐንገት እንደሚደርስም የውሃ ሙላት
ነው፤
መንግሥታትን በጥፋት ወንፊት ያበጥራቸዋል፤
በሕዝቦችም መንጋጋ፣
መንገድ የሚያስት ልጓም ያስገባል::
[29]በሌሊት የተቀደሰ በዓል ስታከብሩ
እንደምትዘምሩ፣
ትዘምራላችሁ፤
ወደ *እግዚአብሔር* ተራራ፣
ወደ እስራኤል ዐለት፣
ሰዎች ዋሽንት እየነፉ በደስታ እንደሚወጡ፣
የእናንተም ልብ እንዲሁ ሐሤት ያደርጋል::
[30]*እግዚአብሔር* በሚነድ ቍጣና በሚባላ እሳት፣
በወጀብና በነጐድጓድ፣ በበረዶም ድንጋይ፣
ግርማ የተሞላበትን ድምፁን ሰዎች እንዲሰሙ
አድርጎ ያሰማል፤
ክንዱም ስትወርድ ያሳያቸዋል::
[31]*የእግዚአብሔር* ድምፅ አሦርን ያስደነግጣል፤
በትሩም ይመታቸዋል::
[32]*እግዚአብሔር* የሚያወርድባቸው የቅጣት
በትር ሁሉ፣
በከበሮና በበገና ድምፅ የታጀበ ነው፤
በጦርነትም ክንዱን እያሳየ ይመታቸዋል::
[33]ከቀድሞ ጀምሮ ቶፌት የተባለ የማቃጠያ
ስፍራ ተዘጋጅቶአል፤
ለንጉሡም ተበጅቶአል፤
ማንደጃ ጒድጓዱም ሰፊና ጥልቅ ነው፤
በውስጡም ብዙ እሳትና ማገዶ አለ፤
*የእግዚአብሔርም* እስትንፋስ
እንደ ፈሳሽ ድኝ ያቀጣጥለዋል::

## በግብጽ ለሚደገፉ ወዮውላቸው

**31** ወደ እስራኤል ቅዱስ ለማይመለከቱ፣
*ከእግዚአብሔርም* ርዳታን ለማይሹ፣
ነገር ግን፤ ለርዳታ ብለው ወደ ግብፅ ለሚወርዱ፣
በፈረሶች ለሚታመኑ፣
በሠረገሎቻቸው ብዛት፣
በፈረሶቻቸውም ታላቅ ብርታት ለሚመኩ
ወዮላቸው!
[2]እርሱም ግን ጠቢብ ነው፤ ጥፋትን ያመጣል፤
ቃሉን አያጥፍም::
በክፉ አድራጊዎች ቤት ላይ፣
በደለኞችንም በሚረዱ ላይ ይነሣል::
[3]ግብፃውያን ሰዎች እንጂ ስምባክ አይደሉም፤
ፈረሶቻቸውም ሥጋ እንጂ መንፈስ አይደሉም፤

30፥22 ዘፀ32፥4፤ ዘሌ15፥19-23፤ ኢዮ22፥24፤ ኢሳ17፥8፤31፥7፤ ሕዝ7፥19-20
30፥23 ዘዳ28፥12፤ ኢዮ36፥31፤ መዝ65፥13፤ኢሳ25፥6፤ 28፥5፤55፥2፤62፥8፤ 65፥21-22፤ኤር31፥14
30፥24 ኢዮ6፥5፤ ኢሳ32፥14፡20፤ ማቴ3፥12፤ሉቃ3፥17
30፥25 ዘፀ17፥6፤ ኢሳ2፥15፤13፥5፤32፥2፤ 34፥6፤41፥18፤65፥12፤ ኤር25፥32፤50፥27፤ ኢል3፥18፤ዘካ14፥8
30፥26 ዘዳ32፥39፤ 2ዜና7፥14፤ መዝ107፥20፤ ኢሳ1፥5፤24፥23፤ 60፥19-20፤ኤር3፥22፤ 17፥14፤ሆሴ14፥4፤ ዘካ14፥7፤ራእ21፥23፤ 22፥5
30፥27 ቍ30፤ 1ነገ18፥24፤ኢዮ41፥21፤ መዝ20፥1፤ኢሳ10፥5፤ 13፥5፤26፥20፤59፥19፤ 64፥2፤66፥14፤ሕዝ22፥31
30፥28 2ነገ19፥28፤ መዝ50፥3፤ኢሳ8፥8፤ 11፥4፤28፥15፤አሞ9፥9
30፥29 ዘኍ49፥24፤ 1ሳሙ10፥5፤ መዝ42፥4፤ኢሳ12፥1፤ 25፥6፤ማቴ26፥30
30፥30 ቍ27፤ ዘፀ9፥18፤20፥18፤ መዝ29፥3፤68፥33፤ ኢሳ4፥4፤9፥12፤10፥25፤ 40፥10፤47፥14፤ 51፥9፤52፥10፤53፥1፤ 59፥16፤62፥8፤63፥12
30፥31 ኢሳ10፥5፡12፤ 11፥4
30፥32 ዘፀ15፥20፤ ኢሳ10፥26፤11፥15፤ ሕዝ32፥10
30፥33 ዘፍ19፥24፤ዘፀ15፥10፤2ሳሙ22፥16፤2ነገ23፥10፤ኢሳ1፥31፤ ራእ9፥17 31፥1 ዘዳ17፥16፤20፥1፤ኢዮ6፥10፤ምሳ21፥31፤ኢሳ1፥4፤ 2፥7፤9፥13፤28፥1፤30፥2፡5፡12፡16፤ኤር37፥5፤46፥9፤ሕዝ29፥16
31፥2 ዘኍ23፥19፤መዝ92፥5፤ምሳ19፥21፤ኢሳ1፥4፤29፥15፤32፥6፤ 45፥7፤47፥11፤ አሞ3፥6፤ሮሜ16፥27

ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (ከ29፥24 ጋርም ያነጻጽሩ)::

30፥22 *ምስሎችህን ታዋርዳለህ፤* በ2፥20 ላይ እንደ ተገለጸው ተስፋ መቍረጥ ሳይሆን፣ በንስሓ ለማለት ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)::

30፥23 *ዝናብ ... ፍሬ ምርጥና የተትረፈረፈ፤* በዘዳ 28፥11-12 ላይ ከተገለጡት የኪዳን በረከቶች ከፊሉ ነው፤ 5፥6 እና ማብ ይመ:: *በዚያ ቀን፤* ከ29፥18 ጋር ያነጻጽሩ:: የ10፥20፡27፤ 26፥1 ማብ ይመ:: *ከብቶችህ ... ይሰማራሉ፤* ከ32፥20 ጋር ያነጻጽሩ::

30፥24 *ድርቆሽ፤* በሚገባ የተዘጋጀ ደረቅ ገፈራ::

30፥25 *በታላቁ የዕልቂት ቀን፤* ከ24፥1፤ 34፥2፡6 ጋር ያነጻጽሩ:: ለአሦር መውደቅ (ቍ 31) አንዱ ማስረጃ ነው:: *ከፍ ባለውም ኰረብታ ሁሉ ላይ ወራጅ ወንዝ፤* የኤደን ገነትን ሁኔታ የመሰለ ሕይወት ወደ ምድሪቱ ይመለሳል ማለት ነው (41፥18፤ መዝ 104፥13-15 ይመ)::

30፥26 *ጨረቃ ... ታበራለች፤* ጨለማው ያልፋል፤ ሌሊቱ እንደ ቀን ይሆናል፤ የቀኑም ብርሃን በሰባት ዕጥፍ ይጨምራል:: *ስብራት ሲጠግን፤ ያቈሰለውንም ሲፈውስ፤* ከሕዝቡ ኀጢአት የተነሣ እስራኤል በፖለቲካው በትር ደቃ ነበር (1፥6፡61፥1፤ ኤር 33፥6 ይመ)::

30፥27 *ስም፤* የእግዚአብሔር መገለጥ፣ በተለይም በኀይሉና በክብሩ ሲገለጥ:: *ቍጣ... ከሚትጒለጒል የጢስ ደመና፤* እግዚአብሔር ራሱን በተለያየ መልክ ለሰዎች ገልጦአል፤ ይገልጣልም፤ እዚህም ላይ ራሱን በማዕበል መስሎ ገልጾአል (ቍ 30፤ 28፥2፤ 29፥6፤ መዝ 18፥7-15 እና ማብ ይመ):: *የሚባላ እሳት፤* ምናልባት መብረቅ ይሆናል::

30፥28 *እስከ ዐንገት እንደሚደርስም፤* በ8፥8 ላይ የአሦር ሰራዊት ሁኔታ በተመሳሳይ መንገድ ተገልጾአል (የዚያኑ ማብ ይመ):: *ልጓም፤* ከ37፥29 ጋር ያነጻጽሩ::

30፥29 *የተቀደሰ በዓል ስታከብሩ እንደምትዘምሩ፤* በ31፥5 ላይ የተጠቀሰውን የፋሲካ በዓል የሚገልጥ ሊሆን ይችላል (ከማቴ 26፥30 ጋር ያነጻጽሩ):: *ወደ እግዚአብሔር ተራራ፤* ቤተ መቅደሱ ያለበትን ጽዮንን ያመለክታል (2፥2-4 እና ማብ ይመ):: *ዐለት፤* እግዚአብሔር ራሱ ነው (17፥10 እና ማብ ይመ)::

30፥30-31 *ድምፅ፤* የዘፀ 20፥18-19፤ መዝ 29፥3-4 እንደ ተጠቀሰው ከነጐድጓድ ጋር የተያያዘ ነው::

30፥30 *ክንዱም ስትወርድ፤* 9፥12፡17፡21፤ 51፥9 እና ማብ ይመ:: *በወጀብና ... በበረዶም ድንጋይ፤* 28፥2 ይመ::

30፥31 *የእግዚአብሔር ድምፅ ... ያስደነግጣል፤* ከመዝ 29፥5-9 ጋር ያነጻጽሩ::

30፥32 *የቅጣት በትር፤* 11፥4 እና ማብ ይመ:: *በከበሮና በበገና ድምፅ፤* ከታላቅ ድል በኋላ ሴቶች በመዝሙርና በጭፈራ ደስታቸውን ይገልጡ ነበር (ዘፀ 15፥20-21፤ 1ሳሙ 18፥6 ይመ)::

30፥33 *ቶፌት፤* ከኢየሩሳሌም ቅጥር ውጭ ሞሎክ ለሚባለው የአሞናውያን ጣዖት አምላክ ሕፃናት የተሠዉበት ስፍራ ነው (2ነገ 23፥10፤ ኤር 7፥31-32፤19፥6፡11-14፤ 1ነገ 11፥7 ይመ):: ስለዚህ የእሳት ማንደጃና ማቃጠያ ስፍራ ተባለ:: *ንጉሡ፤* የአሦር ንጉሥ ነው:: *እንደ ፈሳሽ ድኝ፤* 1፥31፤ ዘፍ 19፥14 እና ማብ ይመ::

*31፥1፤* 30፥1 እና ማብ ይመ:: ምዕራፍ 31 የምዕራፍ 30 ተከታይ ነው:: *ወደ ግብፅ ለሚወርዱ፤* ዘፍ 26፥2 ይመ:: *በፈረሶች ... በሠረገሎቻቸው፤* ግብፅ እጅግ ብዙ ፈረሶችና ሠረገሎች ነበሯት (1ነገ 10፥28-29 ይመ):: *ወደ እስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4 እና ማብ ይመ::

*31፥2፤ እርሱም ግን ጠቢብ ነው፤* በ29፥14-16 እንደ ተጠቀሰው ሕዝቡ በእግዚአብሔር ጥበብ ላይ ጥርጥር ነበረው::

እግዚአብሔር እጁን ሲዘረጋ፣
ረዳታ ሰጪው ይሰናከላል፤
ተረጂውም ይወድቃል፤
ሁለቱም በአንድ ላይ ይጠፋሉ።

[4]እግዚአብሔር እንዲህ ብሎኛል፤
"አንበሳ ወይም የአንበሳ ደቦል
የሰበረውን ይዞ ሲያገሣ፣
ብዙ እረኞች
ተጠራርተው ሲመጡበት፣
ጩኸታቸው እንደማያስፈራው፣
በድምፃቸውም እንደማይታወክ፣
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
በጽዮን ተራራና በከፍታዎቿ ላይ ለውጊያ
እንዲሁ ይወርዳል።
[5]በዐናት ላይ እንደሚያንዣብቡ ወፎች፣
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ኢየሩሳሌምን
እንዲሁ ይጋርዳታል፤
ይከልላታል፤ ይታደጋታል፤
በላይዋ ያልፋል፤ ያድናታልም።"

[6]እናንተ እስራኤላውያን ሆይ፤ እጅግ ወዳመፃችሁበት ወደ እርሱ ተመለሱ። [7]በዚያ ቀን በኀጢአት የተሞላ እጃችሁ የሠራቻውን የወርቅና የብር ጣዖቶች ሁላችሁም ትጥላላችሁና።

[8]"አሦር የሰው ባልሆነ ሰይፍ ይወድቃል፤
የሥጋ ለባሽ ያልሆነም ሰይፍ ይበላዋል።
ከሰይፍ ፊት ይሸሻል፤
ጕልማሶቹም የግዳጅ ሥራ ይሠራሉ።
[9]ጠንካራ ምሽጉ በሽብር ምክንያት ይወድቃል፤
መሪዎቹም የጦር ዐርማ ሲያዩ በድንጋጤ
ይዋጣሉ"
ይላል እሳቱ በጽዮን፣
ማንደጃውም በኢየሩሳሌም የሆነ እግዚ
አብሔር።

## የጽድቅ መንግሥት

**32** እነሆ፤ ንጉሥ በጽድቅ ይነግሣል፤
ገዦችም በፍትሕ ይገዛሉ።
[2]እያንዳንዱ ሰው ከነፋስ መከለያ፣
ከወጀብም መጠጊያ ይሆናል።
በበረሓም እንደ ውሃ ምንጭ፣
በተጠማም ምድር እንደ ትልቅ ቋጥኝ ጥላ
ይሆናል።
[3]የሚያዩ ሰዎች ዐይን ከእንግዲህ አይጨፈንም፤
የሚሰሙም ጆሮዎች ነቅተው ያዳምጣሉ።
[4]የችኵል አእምሮ ያውቃል፤ ያስተውላልም፤
የተብታባም ምላስ የተፈታ ይሆናል፤
አጥርቶም ይናገራል።
[5]ከእንግዲህ ሰነፍ ጨዋ አይባልም፤
ጋጠወጥም አይከበርም።
[6]ሰነፍ ስንፍናን ይናገራል፤
አእምሮው ክፋትን ያውጠነጥናል፤
ፈሪሀ እግዚአብሔር የሌለበትን አድራጐት
ይፈጽማል፤
በእግዚአብሔርም ላይ የስሕተት ቃል
ይናገራል፤
ለተራበ ምግብ ይከለክላል፤
ለተጠማ ውሃ አይሰጥም።
[7]የጋጠወጥ ዘዴ ክፉ ነው፤
የችግረኛም አቤቱታ ትክክል ቢሆን፣
ድኻን በሐሰት ለማጥፋት፣
ክፋት ያውጠነጥናል።
[8]ጨዋ ግን ሐሳቡም ጨዋ ነው፤
በጨዋነት ምግባርም ጸንቶ ይገኛል።

## የኢየሩሳሌም ሴቶች

[9]እናንት ትዕቢት የወጠራችሁ ሴቶች፣
ተነሡ፤ ድምፄን ስሙ፤
እናንት ተደላድላችሁ የምትኖሩ፣ ሴቶች ልጆች
ሆይ፤
የምነግራችሁን አድምጡ።
[10]ዓመቱ ገና እንዳለፈ፣
ተደላድላችሁ የነበራችሁ ትንቀጠቀጣላችሁ፤
የወይን ተክል ፍሬ አይሰጥም፤
የፍራፍሬም ወቅት አይመጣም።

31፥3 ነህ1፥10፤ ኢዮ30፥21፤መዝ9፥20፤ ኢሳ9፥17:21፤10፥3፤ 20፥5:6፤30፥5-7:16፤ 36፥9፤ኤር17፥5፤ 51፥25፤ሕዝ20፥34፤ 28፥9፤2ተሰ2፥4
31፥4 ዘኍ24፥9፤ 1ሳሙ17፥34፤ መዝ74፥23፤ኢሳ42፥13፤ ኤር3፥15፤23፥4፤ ሕዝ34፥23፤ ሆሴ11፥10፤አሞ3፥8፤ ናሆ3፥18
31፥5 ዘዳ1፥2፤ ዘፀ12፥23፤መዝ34፥7፤ 91፥4፤ኢሳ5፥2፤37፥35፤ 38፥6፤ዘካ9፥15፤ ማቴ23፥37
31፥6 ኢዮ22፥23፤ ኢሳ1፥5:27
31፥7 መዝ135፥15፤ ኢሳ29፥18፤30፥22
31፥8 ዘፍ49፥15፤ ዘፀ12፥12፤ዘዳ20፥11፤ ኢሳ10፥12፤14፥25፤ 27፥1፤33፥1፤37፥7፤ ኤር25፥12፤ዕን2፥8
31፥9 ዘዳ32፥31: 37፤መዝ21፥9፤ ኢሳ10፥17፤18፥3፤ ኤር4፥6፤51፥9፤ ናሆ3፥7፤ሚል4፥1
32፥1 መዝ72፥1-4፤ 149፥2፤ኢሳ6፥5፤ 9፥7፤ 28፥6፤55፥4፤ ሕዝ37፥24
32፥2 1ነገ18፥4፤ መዝ23፥2፤55፥8፤ 107፥35፤ኢሳ30፥25፤ 44፥3፤49፥10፤ ኤር31፥9
32፥3 ዘዳ29፥4፤ ኢሳ29፥18፤35፥5፤ 42፥7:16
32፥4 ኢሳ6፥10፤ 29፥24፤35፥6
32፥5 1ሳሙ25፥25
32፥6 ምሳ19፥3፤ 24፥2፤ኢሳ3፥12:15፤ 9፥16:17፤26፥10
32፥7 መዝ72፥4፤ ኢሳ29፥19:20:21፤ 61፥1፤ኤር5፥26-28፤ ዳን12፥10፤ሚክ7፥3
32፥8 1ዜና29፥9፤ ምሳ11፥25፤ኢሳ14፥24
32፥9 ቍ11፤ኢሳ4፥1፤ 28፥23፤47፥8፤ዳን4፥4፤አሞ6፥1፤ሶፎ2፥15
32፥10 ኢሳ5፥5-6፤ 24፥7፤37፥30

31፥31 *እጁን ሲዘረጋ፤* ከ5፥25፤ 9፥12:17:21፤ 10፥4 ጋር ያነጻጽሩ። *ረዳታ ሰጪው ይሰናከላል፤* ከ30፥3:5 ጋር ያነጻጽሩ።

31፥4 *አንበሳ፤* ተነጻጻሪ ዘይቤ ነው፤ ነገር ግን ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ የአሦርን ንጉሥ ያመለክት ይሆናል (የ15፥9 ማብ ይመ)። *እረኞች፤* የአሕዛብን ገዦዎች ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ ለመግለጽ የገባ ቃል ነው (ናሆ 3፥18 ይመ)።

31፥5 *ወፎች ... ይጋርዳታል፤* ከዘዳ 32፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ። *በላይዋ ያልፋል፤* በግብፅ በየበሩ ጉብን ላይ ያለውን ደም እየተመለከተ፣ ዐልፎ ይሄድ የነበረውን ቀሳፊ መልአክ በተዘዋዋሪ መንገድ ሲያስታውስ፣ "ፋሲካ" የሚለውን ቃል ያሳስባል (ዘፀ 12፥13:23 ይመ)፤ ከኢሳ 37፥35 ጋር ያነጻጽሩ።

31፥6 *ክፉኛ ወዳመፃችሁበት፤* 1፥2 እና ማብ ይመ።

31፥7 *ጣዖቶች ... ትጥላላችሁና፤* 2፥20 እና ማብ ይመ።

31፥8 *የሰው ባልሆነ ሰይፍ፤* የእግዚአብሔር መልአክ 185,000 ወታደሮችን መትቶ ጣለ (37፥36 ይመ)። *የግዳጅ ሥራ ይሠራሉ፤* እንደ ጦር ምርኮኞች ማለት ነው።

31፥9 *ምሽጉ፤* ነነዌ በ612 ዓ.ቅ.ክ በሜዶንና በባቢሎናውያን ተደመሰሰች (ናሆ 3፥7 ይመ)። *መሪዎቹም ... ይዋጣሉ፤* ከናሆ 2፥10 ጋር ያነጻጽሩ። *እሳቱ ... ማንደጃውም፤* የእግዚአብሔር ክብር በጽዮን ያድራል፤ ከዚያም ለሕዝቡ ማዕከል ከሆነው ስፍራ ፍርዱ በክፉዎች ላይ ይወጣል (10፥17፤ 30፥33፤ ከዘሌ 10፥2፤ ኢል 3፥16፤ አሞ 1፥2 ጋር ያነጻጽሩ)።

32፥1 *ንጉሥ በጽድቅ፤* የመሲሑን ዘመን እንደ ገና ያሳያል (9፥7፤ 11፥4፤ 16፥5 እና ማብ ይመ)። ከቍ 16-17፤ 33፥17 ጋር ያነጻጽሩ።

32፥2 *እያንዳንዱ ሰው፤* እግዚአብሔር የተቤዣቸው ወገኖች የመከላከያና የበረከት ምንጭ በመሆን እግዚአብሔርን የሚያንጸባርቁ ይሆናሉ (ቍ 3-8 ይመ)። *መከለያ ... መጠጊያ ... ጥላ፤* እግዚአብሔርን በተመለከተ ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ አገላለጽ በ25፥4 ላይ ይገኛል (4፥5-6 እና ማብ ይመ)። *በበረሓም እንደ ውሃ ምንጭ፤* 35፥6-7፤ 41፥18፤ 49፥10 ይመ።

32፥3 *ዐይን ... አይጨፈንም ... ጆሮዎች ነቅተው ያደምጣሉ፤* 35፥5 እና ማብ ይመ (ከ6፥9-10 ጋር ያነጻጽሩ)።

*32፥5-8፤* እግዚአብሔር የተቤዣቸው ከእንግዲህ በአላዋቂዎች መካከል አይኖሩም። በአላዋቂና በጠቢብ ወይም በጨዋ ሰው መካከል ያለውን ንጽጽር ማሳየት የጥበብ መጻሕፍት ዐይነተኛ ባሕርይ ነው (ምሳ 9፥1-6 ከምሳ 9፥13-18 ጋር ያነጻጽሩ)።

32፥6 *ሰነፍ ስንፍናን ይናገራል፤* 9፥16-17፤ ከመዝ 14፥1፤ 53፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

32፥7 *የችግረኛ አቤቱታ፤* 1፥17እና ማብ ይመ።

32፥8 *በጨዋነት ... ጸንቶ ይገኛል፤* 8፥10 እና ማብ ይመ።

32፥9 *ሴቶች፤* ከ3፥16-4፥1 ጋር ያነጻጽሩ። *ትዕቢት የወጠራችሁ ... ተደላድላችሁ የምትኖሩ፤* ቍ11፤አሞ 6፥1ይመ።

32፥10 *ዓመት፤* በ701 ዓ.ቅ.ክ ላይ የተፈጸመውን የሰናክሬም ወረራ የሚያሳይ ይመስላል። *የወይን ተክል ፍሬ አይሰጥም፤*

[11]እናንት ትዕቢት የወጠራችሁ ሴቶች
ተንቀጥቀጡ፤
እናንት ተደላድላችሁ የምትኖሩ ሴቶች
ልጆች፤ በፍርሀት ተርበትበቱ፤
ልብሳችሁን አውልቁ፣
ወገባችሁን በማቅ ታጠቁ።
[12]ስለ ለሙ መሬት ደረታችሁን ምቱ፤
ስለ ፍሬያማው የወይን ተክል ዕዘኑ፤
[13]ስለ ሕዝቤ ምድር፣
እሾኽና አሜከላ ስለ በቀለበት ምድር፣
ስለ ፈንጠዝያ ቤቶች ሁሉ፣
ስለዚህችም መፈንጫ ከተማ አልቅሱ።
[14]ዐምባ ምሽጉ ወና ይሆናል፤
ውካታ የበዛበት ከተማ ጭር ይላል፤
ምሽጉና ማማው ለዘላለሙ ዋሻ፣
የዱር አህያ መፈንጫ፣ የመንጋም መሰማሪያ
ይሆናል፤
[15]ይህም የሚሆነው መንፈስ ከላይ እስኪፈስልን፣
ምድረ በዳው ለም መሬት፣
ለሙ መሬትም ጫካ እስኪመስል ድረስ ነው።
[16]በምድረ በዳ ፍትሕ ይሰፍናል፤
በለሙም መሬት ጽድቅ ይኖራል፤
[17]የጽድቅ ፍሬ ሰላም፣
የጽድቅ ውጤትም ጸጥታና ለዘላለም መታመን
ይሆናል።
[18]ሕዝቤ ሰላማዊ በሆነ መኖሪያ፣
በሚያስተማምን ቤት፣
ጸጥ ባለም ስፍራ ዐርፎ ይኖራል።
[19]ደኑ በበረዶ ቢመታ፣
ከተማውም ፈጽሞ ቢወድም፣
[20]በየወንዙ ዳር ዘር የምትዘሩ፣
በሬዎቻችሁንና አህዮቻችሁን በነጻነት
የምታሰማሩ፣
ምንኛ የተባረካችሁ ናችሁ።

## የጭንቅ ጊዜና ርዳታ

**33** አንተ ሳትጠፋ የምታጠፋ፣
አንት አጥፊ፣ ወዮልህ!
አንተ ሳትካድ የምትክድ፣
አንት ከዳተኛ፣ ወዮልህ!
ማጥፋትን በተውህ ጊዜ፣
ትጠፋለህ፤
ክሕደትህንም በተውህ ጊዜ
ትከዳለህ።
[2]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ማረን፤
አንተን ተስፋ አድርገናል።
በየማለዳው ብርታት፣
በጭንቅ ጊዜም ድነት ሁነን።
[3]ሕዝቦች በድምፅህ ነጐድጓድ ይሸሻሉ፣
መንግሥታት ስትነሣ ይበተናሉ።
[4]ሕዝቦች ሆይ፤ አንበጣ እንደሚሰበስብ
ብዝበዛችሁም ይሰበሰባል፤
ሰዎችም እንደ ኩብኩባ ይጨፍሩበታል።
[5]*እግዚአብሔር* በአርያም ተቀምጦአልና ከፍ
ከፍ አለ፤
ጽዮንን በጽድቅና በፍትሕ ይሞላታል።
[6]እርሱ ለዘመንህ የሚያስተማምን መሠረት፣
የድነት፣ የዕውቀትና የጥበብ መዝገብ
ይሆናል፤
እግዚአብሔርንም መፍራት የዚህ ሀብት
ቍልፍ ነው[ሀ]።
[7]እነሆ፤ ጐበዞቻቸው በየመንገዱ ይጮኻሉ፤
የሰላም መልእክተኞችም አምርረው ያለቅሳሉ።
[8]አውራ ጐዳናዎች ባዶ ናቸው፤
በመንገድ ላይ ሰው የለም፤
ስምምነቱ ፈርሶአል፤
መካሪዎቹ[ለ] ተንቀዋል፤
የሚከበርም የለም።

32፥11 ቍ9፤ ኢሳ3፥24፤ኢሳ33፥14፤ 47፥2፤ሚክ1፥8፤ ናሆ3፥5
32፥12 ኢሳ16፥9፤ ናሆ2፥7
32፥13 ኢሳ5፥6፤ 23፥7፤24፥11፤ ሆሴ10፥8
32፥14 መዝ104፥11፤ ኢሳ2፥15፤5፥17፤ 6፥11፤13፥22፤27፥10፤ 34፥13
32፥15 መዝ107፥35፤ ኢሳ11፥2፤29፥17፤ 35፥1-2፤ሕዝ37፥9
32፥16 መዝ48፥1፤ ኢሳ1፥26፤9፥7፤28፥6፤ 35፥1፡6፤42፥11
32፥17 መዝ85፥10፤ 119፥165፤ኢሳ9፥7፤ 30፥15፤ሮሜ14፥17፤ ዕብ12፥11፤ያዕ3፥18
32፥18 ኢሱ1፥13፤ ኢዮ11፥18፤ኢሳ2፥4፤ 26፥1፤33፥20፤37፥33፤ 65፥21፤66፥14፤ ሆሴ2፥18-23፤ አሞ9፥14
32፥19 ኢዮ40፥11፤ ኢሳ10፥19፤19፥18፤ 24፥10፤27፥10፤ 28፥17፤ዘካ11፥2
32፥20 ዘዳ28፥12፤ ኢዮ39፥8፤መክ11፥1፤ ኢሳ30፥24
33፥1 2ነገ19፥21፤ ኢሳ21፥2፤28፥1፤ 31፥8፤ኤር30፥16፤ ሕዝ39፥10፤ማቴ7፥2
33፥2 ዘፍ43፥29፤ ዕዝ9፥8፤መዝ13፥5፤ ኢሳ5፥30፤12፥2፤ 40፥10፤51፥9፤59፥16፤ 63፥5
33፥3 ቍ10፤ ዘኍ10፥35፤ መዝ12፥5፤46፥6፤ 68፥1፡33፤ኢሳ13፥14፤ 59፥16-18
33፥4 ዘኍ14፥3፤ 2ነገ7፥16፤ኢሳ17፥5፤ ኢል1፥4፤3፥13
33፥5 ኢዮ16፥19፤ኢሳ1፥26፤ 5፥16፤9፥7፤28፥6
33፥6 ዘፍ39፥3፤ ኢዮ22፥25፤ምሳ1፥7፤ኢሳ11፥2-3፤12፥2፤26፥1፤ 51፥6፤60፥18፤ማቴ6፥33
33፥7 2ነገ18፥37፤ኢሳ10፥34
33፥8 መሳ5፥6፤2ነገ18፥14፤ኢሳ30፥21፤35፥8፤60፥15፤ዘካ7፥14

[ሀ]6 ወይም እግዚአብሔርን መፍራት ከእግዚአብሔር የሆነ ሀብት ነው
[ለ]8 የሙት ባሕር ጥቅሎች ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ ከተሞች ይላል።

ከ37፥30 ጋር ያነጻጽሩ። የአሦር ሰራዊት ብዙ ጥፋት የሚያደርስ በመሆኑ የበጋው ፍሬ ሁሉ ይበላሻል።

32፥11 *አውልቁ፤* ከ47፥2-3 ጋር ያነጻጽሩ። *ማቅ፤* ከ3፥24፤ 22፥12 ጋር ያነጻጽሩ፤ የዘፍ 37፥34 ማብ ይመ።

32፥12 *ደረታችሁን ምቱ፤* በናሆም 2፥7 ላይ እንደ ተጠቀሱት እንደ ነነዌ ሴት ባሪያዎች ማለት ነው። *ስለ ፍሬያማው የወይን ተክል፤* ይህን ሐዘን በ16፥9 ላይ ከተገለጸው ጋር ያነጻጽሩ።

32፥13 *እሾህና አሜከላ፤* 5፥6፤ 7፥23 እና ማብ ይመ። *ደስታ ... የፈንጠዝያ፤* 22፥2 እና ማብ ይመ፤ ከኤር 16፥8-9 ጋር ያነጻጽሩ።

32፥14 *ውካታ የበዛበት ከተማ ... ምሽጉና፤* የአሦር ወረራ ኢየሩሳሌም አንድ ቀን እንደምትደመሰስ የማስጠንቀቂያ ምልክት ነበር (24፥10 እና ማብ ይመ)። *የዱር አህያ ... የመንጋም፤* ከ7፥25፤ 13፥21-22፤ 34፥13 ጋር ያነጻጽሩ።

32፥15 *መንፈስ ከላይ፤* የመንፈስ ቅዱስ መፍሰስ ከበረከት መትረፍረፍ ጋር የተያያዘ መሆኑ በ44፥3 ላይ ተገልጾአል (ቍ 2፤ 11፥2 እና ማብ፤ ኢል 2፥28-32 ይመ)። *ለሙ መሬትም ጫካ፤* ምናልባት ሊባኖስ ሳይሆን አይቀርም (29፥17 እና ማብ ይመ፤ ከ35፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ)።

32፥16 *ፍትሕ ... ጽድቅ፤* ቍ 1 እና ማብ ይመ።

32፥17 *ሰላም፤* ከ9፥7፤ 11፥6-9 ጋር ያነጻጽሩ። *ጸጥታና ... መታመን፤* ከ30፥15 ጋር ያወዳድሩ።

32፥18 *በሚያስተማምን ...ጸጥ ባለም፤* የቍ9 ማብ ይመ። *ዐርፎ ይኖራል፤* 28፥12 እና ማብ ይመ።

32፥19 *ደኑ፤* ምናልባት አሦር ይሆናል። 10፥33-34 እና ማብ ይመ። *በረዶ፤* ከ28፥2 ጋር ያነጻጽሩ። *ከተማውም፤* 24፥10 እና ማብ ይመ።

*32፥20፤* እዚህ ላይ በጌታ ቀን የሚኖረው የተትረፈረፈ በረከት ተገልጾአል (30፥23-24 እና ማብ ይመ)።

33፥1 *ወዮልህ!* የ28፥1-35፥10 ማብ ይመ። *አጥፊ ... ከዳተኛ፤* ምናልባት አሦርን ይሆናል (10፥5-6፤ 16፥4፤ 21፥2፤ 24፥16 እና ማብ ይመ)።

33፥2-9 አሦር እንደሚጠፋ አስቀድሞ የተነገረውን እንዲፈጽመው እግዚአብሔርን በጸሎት የሚጠይቅ ክፍል ነው።

33፥2 *ማረን፤* 30፥18እና ማብ ይመ። *ብርታት ... ድነት፤* 12፥2 እና ማብ ይመ። ከ59፥16 ጋር ያነጻጽሩ። *በጭንቅ፤* 37፥3 ይመ።

33፥3 *በድምፅህ ነጐድጓድ፤* 30፥30-31 እና ማብ ይመ። *ስትነሣ ይበተናሉ፤* ዘኍ 10፥35ን ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ ይገልጣል፤ ከመዝ 68፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

33፥5 *በጽድቅና ... ይሞላታል፤* 1፥26፤ 32፥1 እና ማብ ይመ።

33፥6 *የዕውቀትና የጥበብ ... እግዚአብሔርንም መፍራት፤* በ11፥2 ላይ ከመሲሑ ጋር የተያያዙ ቃላት ናቸው፤ 9፥6፤ ምሳ 1፥7 እና ማብ ይመ።

33፥7 *ጐበዞቻቸው፤* በ701 ዓ.ቅ.ክ ሰናክሬም አገሪቱን በወረረ ጊዜ በጀግንነት የታገሉ የይሁዳ ሰዎች ናቸው (10፥28-34 ይመ)። *የሰላም መልእክተኞችም፤* ከአሦር የጦር አዛዥ ጋር ለመነጋገር የሄዱ ሦስት ሹማምንት (36፥3፡22 ይመ)።

33፥8 *አውራ ጐዳናዎች ባዶ ናቸው፤* በመንገዶቹ መጓዝና መነገድ አልተቻለም ነበር (መሳ 5፥6 ይመ)። *ስምምነቱ፤* ሕዝቅያስ

[9]ምድሪቱ አለቀሰች*፤ መነመነች፤
ሊባኖስ ዐፈረች፤ ጠወለገች፤
ሳሮን እንደ ዐረባ ምድረ በዳ ሆነች፤
ባሳንና ቀርሜሎስ ቅጠላቸውን አረገፉ።
[10]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "አሁን እነሣለሁ፤
አሁን ከፍ ከፍ እላለሁ፤
አሁን እከብራለሁ።
[11]ገለባን ፀነሳችሁ፤
እብቅንም ወለዳችሁ፤
እስትንፋሳችሁም የሚበላችሁ እሳት ነው።
[12]ሕዝቦች ኖራ እንደሚወጣው ድንጋይ ይቃጠላሉ፤
እንደ እሾኽ ቍጥቋጦ በእሳት ይጋያሉ።"

[13]እናንት በሩቅ ያላችሁ ያደረግሁትን ስሙ፤
እናንት በቅርብ ያላችሁ ኀይሌን ዕወቁ!
[14]በጽዮን ያሉ ኀጢአተኞች ደነገጡ፤
አምላክ የሌላቸውም ፍርሀት ይዞአቸው፣
"ከእኛ መካከል ከሚባላ እሳት ጋር ማን
መኖር ይችላል፣
ከዘላለም እሳትስ ጋር ማን መኖር ይችላል?"
አሉ።
[15]በጽድቅ የሚራመድ፣
ቅን ነገር የሚናገር፣
በሽንገላ የሚገኝ ትርፍ የሚንቅ፣
መማለጃን ላለመቀበል እጁን የሚሰበስብ፣
የግድያን ሤራ ላለማስማት ጆሮውን የሚደፍን፣
ክፉትን ላለማየት ዐይኑን የሚጨፍን፣
[16]ይህ ሰው በከፍታ ላይ ይኖራል፤
የተራራም ምሽግ መጠጊያው ይሆናል፤
እንጀራ ይሰጠዋል፣
ውሃውም አይቋረጥበትም።

[17]ዐይኖችህ ንጉሡን በውበቱ ያዩታል፤
በሩቅ የተዘረጋችውንም ምድር ይመለከታሉ።
[18]የቀደመው መከራ ትዝ እያለህ፣
"ያ ዋና አለቃ የት አለ?
ግብር ተቀባዩስ ወዴት ሄደ?
የመጠበቂያ ማማ ኀላፊውስ የት አለ?"
ትላለህ።
[19]እነዚያ ንግግራቸው የማይገባ፣
የሚሉትም የማይታወቅ፣
ሊረዱት የማይቻል ቋንቋ የሚናገሩትን
ጋጠወጥ ሕዝብ ከእንግዲህ አታያቸውም።
[20]በዓላታችንን የምናከብርባትን ከተማ ጽዮንን
ተመልከት፤
ሰላማዊ መኖሪያ፣ የማትነቃነቅ ድንኳን
የሆነችውን፣
ካስማዋ የማይነቀል፣
ከገመዷ አንዱ እንኳ የማይበጠሰውን፣
ኢየሩሳሌምን ዐይኖችህ ያያሉ።
[21]እግዚአብሔር በዚያ ኀይላችን ይሆናል፤
ባለ መቅዘፊያ ጀልባዎች እንደማያልፉባቸው፣
ታላላቅ መርከቦችም እንደማይሻገሯቸው፣
ሰፋፊ ወንዞችና ጅረቶች ይሆንልናል።
[22]እግዚአብሔር ዳኛችን ነው፤
እግዚአብሔር ሕግ ሰጪያችን ነው፤
እግዚአብሔር ንጉሣችን ነው፤
የሚያድነንም እርሱ ነው።
[23]መወጠሪያ ገመድህ ላልቶአል፤
ምሰሶው ጠብቆ አልተተከለም፤
ሸራው አልተወጠረም፤
በዚያ ጊዜ ታላቅ ምርኮ ይከፋፈላል፤

33፥9 1ነገ18፥19፤ 2ነገ19፥23፤ 1ዜና27፥29፤ኢሳ2፥13፤ 3፥26፤15፥6፤35፥2፤ 37፥14፤ኤር22፥6፤ ሚክ7፥14፤ናሆ1፥4
33፥10 ቍ3፤ ኢሳ2፥21፤5፥16
33፥11 መዝ7፥14፤ ኢሳ1፥31፤26፥18፤ 59፥4፤ያዕ1፥15
33፥12 ኢሳ5፥6፤ 10፥17፤27፥11፤ አሞ2፥1
33፥13 መዝ48፥10፤ 49፥1፤ኢሳ34፥1፤ 48፥16፤49፥1
33፥14 ኢሳ1፥28፡ 31፤30፥30፤32፥11፤ ዘካ13፥9፤ዕብ12፥29
33፥15 መዝ15፥2፤ 24፥4፤119፥37፤ ምሳ15፥27፤ኢሳ58፥8፤ ሕዝ22፥13፤33፥31
33፥16 ዘዳ32፥13፤ መዝ18፥1-2፤46፥1፤ ኢሳ25፥4፤26፥1፤ 48፥21፤49፥10፤ 65፥13
33፥17 ኢሳ4፥2፤ 6፥5፤26፥15
33፥18 ኢሳ2፥15፤ 17፥14
33፥19 ዘፍ11፥7፤ መዝ5፥5፤ኢሳ28፥11
33፥20 ቍ6፤ ዘፍ26፥22፤መዝ46፥5፤ 125፥1፤ኢሳ32፥18
33፥21 ዘፀ17፥6፤ መዝ1፥3፤ኢሳ10፥34፤ 23፥1፤32፥2፤41፥18፤ 48፥18፤49፥10፤ 66፥12፤ናሆ3፥8
33፥22 መዝ89፥18፤ ኢሳ2፥3፤ 11፥4፤25፥9፤ ያዕ4፥12
33፥23 2ነገ7፥8፡16

*9 *ወይም ደረቀች (ጠወለገች)*

ለሰናክሬም ከፍተኛ ገንዘብ ለመክፈል በተስማማ ጊዜ የተደረገ ውል ነው (2ነገ 18፥14)።

33፥9 *ምድሪቱ ... መነመነች፤* የዕርሻና የግጦሽ መሬት በወራሪዎች ተበላሽቶና ጠፍቶ ነበር፤ 24፥4 እና ማብ ይመ። *ሊባኖስ፤* በዝግባዋና (2፥13) በእንስሳቷ (40፥16) የታወቀች ናት። *ሳሮን፤* ከኢዮጴ በስተ ሰሜን በሜድትራኒያን ጠረፍ ላይ የሚገኝ በልምላሜው ውበትና በግጦሹ የሚታወቅ መሬት (35፥2፤ 65፥10፤ 1ዜና 27፥29 ይመ)። *ዐረባ፤* ከዮርዳኖስ ወንዝና ከሙት ባሕር ጋር የተያይዘ ምድረ በዳ (ዘዳ 1፥1፤ 2፥8 ይመ)። *ባሳን፤* 2፥13 እና ማብ ይመ። *ቀርሜሎስ፤* የ1ነገ 18፥19 ማብ ይመ። በ29፥17፤ 32፥15 እንደ ተጠቀሰው "ለም የዕርሻ ቦታ" ወይም በ16፥10 እንደ ተገለጸው "የአትክልት ቦታ" ማለት ነው። አብዛኛውን ጊዜ ካደገና ከለመለመ የግጦሽ ሣር ጋርም ይያያዛል (35፥2፤ ሚክ 7፥4፤ ናሆ 1፥4 ይመ)።

33፥10 *ከፍ ከፍ እላለሁ፤* ባመፀው ሕዝቡ ላይ የሚያመጣውን ፍርድ ያመለክታል (ቍ 13 ይመ)።

33፥11 *ፀነሳችሁ ... ወለዳችሁ፤* ከ26፥18 ጋር ያነጻጽሩ። *እስትንፋሳችሁም የሚበላችሁ እሳት ነው፤* ለመጥፊያቸው የሚሆነውን ነገር ይሠራሉ ማለት ነው።

33፥12 *ኖራ፤* ቃጠሎው የሚያስተርፈው ነገር የለም (አሞ 2፥1 ይመ)። የእሾኽ ቍጥቋጦ እሳት ሲነካው በቶሉ ይቃጠላል (27፥4፤ 2ሳሙ 23፥6-7 ይመ)።

33፥13 *ስሙ ... ዕወቁ፤* ከ34፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

33፥14 *በጽዮን ያሉ ኀጢአተኞች፤* 1፥27-28፤4፥4 ይመ። *ከሚባላ እሳት፤* የፍርድን አምላክ መገኘት ያመለክታል (29፥6፤ 30፥27፡30፤ ዘፀ 24፥17፤ ዘዳ 4፥24፤ 9፥3፤ 2ሳሙ 22፥9፤ መዝ 18፥8፤ ዕብ 12፥29 ይመ)።

*33፥15፤* ተመሳሳይ መስፈርቶች በመዝ 15፥2-5፤ 24፥4 ላይ ይገኛሉ። *መማለጃን፤* 1፥23 ይመ።

33፥16 *በከፍታ ... ምሽግ፤* በእግዚአብሔር የሚገኘውን አስተማማኝ ጸጥታ አመልካች ነው (ከመዝ 18፥1-3 ጋር ያነጻጽሩ)። *እንጀራ ... ውሃውም፤* ከ 49፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

33፥17 *ንጉሡን፤* 32፥1 እና ማብ ይመ፤ ከ6፥5 ጋር ያነጻጽሩ። *በውበቱ፤* የዳዊትን ንግሥና ግርማ ሞገስ የሚያንጸባርቅ ነው። ምናልባት የምትመጣውን መሲሐዊት መንግሥት በምሳሌ የሚያሳይ ሊሆን ይችላል (ከ4፥2፤ መዝ 45፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ፤ ከኢሳ 53፥2 ጋር ያወዳድሩ)። *በሩቅ ... ምድር፤* 26፥15 እና ማብ ይመ።

33፥18 *የቀደመውም መከራ፤* የአሦርን ወረራ የሚያስታውስ ነው (17፥12-14 እና ማብ ይመ)። *ግብር፤* ያለውድ በግዴታ ተሰብስቦ ለመንግሥት የሚገባ ገንዘብ እህል ወዘተ (ቍ 8 እና ማብ ይመ)። *የመጠበቂያ ማማ፤* የይሁዳ ምሽጎች ምናልባት በአሦራውያን ቍጥጥር ሥር ሳይሆኑ አልቀረም (2፥15 ይመ)።

33፥19 *ንግግራቸው የማይገባ፤* ከ10፥12 ጋር ያነጻጽሩ። *የሚሉት ምኑም የማይታወቅ፤* የአሦር ቋንቋ ከዕብራይስጥ ጋር ተመሳሳይ ቢሆንም፣ ለእስራኤላውያን አይገባቸውም ነበር፤ 28፥11፤ ዘፀ 28፥49 ይመ።

33፥20 *በዓላታችንን፤* 1፥14 እና ማብ ይመ። *ጽዮንን ተመልከት፤* በቍ 7-9 ላይ ከተጠቀሰችው ከተማ ጋር የተነጻጸረች፤ የተዋጀችም ከተማ። *ሰላማዊ መኖሪያ፤* 32፥17-18 እና ማብ ይመ። *የማትነቃነቅ ድንኳን፤* የምርኮው ዘመን ያበቃል ማለት ነው። *ካስማዋ ... ከገመድዋ፤* በ54፥2 ስለ ኢየሩሳሌም ከተገለጸው ተመሳሳይ ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ።

33፥21 *ኀይላችን ይሆናል፤* 10፥34 ይመ (ከመዝ 93፥4 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሰፋፊ ወንዞች፤* እንደ ጢሮስ (23፥1) ወይም እንደ ቴብስ (ናሆ 3፥8) ያሉትን ድንበሮች በቀላሉ መሻገር አለመቻሉን ለማመልከት ነው።

33፥22 *ዳኛችን፤* 2፥4፤ 11፥4 እና ማብ ይመ። *ሕግ ሰጪያችን፤* 2፥3፤ 51፥4፤ ዘፍ 49፥10 ይመ። *ንጉሣችን፤* ቍ 17፤ 32፥1 እና ማብ ይመ፤ መዝ 46፥48 ይመ። *የሚያድነንም፤* መሳ 2፥16 ይመ።

33፥23 *መወጠሪያ፤* ኢየሩሳሌም ከአሦር ጋር ለመዋጋት አለመዘጋጀቷን ለመግለጽ በመርከብ ምሳሌነት ቀርባለች። *በዚያን ጊዜ፤*

አንካሳ እንኳ ሳይቀር ምርኮ ይወስዳል::
[24]በጽዮን ተቀምጦ፣ "ታምሜአለሁ" የሚል
አይኖርም፤
በዚያ የሚኖሩ ሰዎች ኀጢአትም ይቅር
ይባላል::

## ፍርድ በአሕዛብ ላይ

**34** እናንት አሕዛብ ሆይ፤ ኑ አድምጡም፤
እናንተ ሰዎች ሆይ፤ አስተውሉ::
ምድርና በውስጧ ያለ ሁሉ፣
ዓለምና ከእርሷ የሚበቅል ሁሉ ይስማ::
[2]እግዚአብሔር አሕዛብን ሁሉ ተቈጥቶአል፤
ቍጣውም በሰራዊታቸው ሁሉ ላይ ነው፤
ፈጽሞ ያጠፋቸዋል[a]፤
ለዕርድም አሳልፎ ይሰጣቸዋል::
[3]ከእነርሱም የተገደሉት ወደ ውጭ ይጣላሉ፤
ሬሳቸው ይከረፋል፤
ተራሮችም ደም በደም ይሆናሉ::
[4]የሰማይ ከዋክብት ሁሉ ይሟሸሻሉ፤
ሰማይ እንደ ብራና ይጠቀለላል፤
የከዋክብት ሰራዊት ሁሉ፣
ጠውልጎ እንደ ረገፈ የወይን ቅጠል፣
ደርቆም እንደ ወደቀ የበለስ ቅጠል
ይሆናሉ::
[5]ሰይፌ በሰማያት እስኪበቃት ጠጥታለች፤
እነሆ፤ ወደ ኤዶም፣
ፈጽሞ ወዳጠፋሁት ሕዝብ ለፍርድ
ወርዳለች::
[6]የእግዚአብሔር ሰይፍ በደም ተነክራለች፤
ሥብ ጠግባለች፤
በበግ ጠቦትና በፍየል ደም፣
በአውራም በግ ኵላሊት ሥብ ተሸፍናለች::
እግዚአብሔር በባሶራ ከተማ መሥዋዕት፣
በኤዶምም ታላቅ ዕርድ አዘጋጅቶአልና::
[7]ጐሽ አብሮአቸው፣
ኮርማም ከወይፈን ጋር ይወድቃል፤
ምድራቸው በደም ትርሳለች፤
ዐፈራቸውም ሥብ በሥብ ይሆናል::
[8]እግዚአብሔር የበቀል ቀን፣
ስለ ጽዮንም የሚሟገትበት ዓመት አለውና::
[9]የኤዶም ምንጮች ሬንጅ፣
ዐፈሯ የሚቃጠል ድኝ፣
ምድሯም የሚንበለበል ዝፍት ይሆናል::
[10]እሳቷ ሌሊትና ቀን አይጠፋም፤
ጢሷም ለዘላለም ይትጐለጐላል፤
ከትውልድ እስከ ትውልድ ባድማ ትሆናለች፤
ማንም በዚያ ዳግም አያልፍም::
[11]ጭልፊትና[b] ጃርት ይወርሷታል፤
ጕጕትና ቍራም ጎጆ ይሠሩባታል::
እግዚአብሔር በኤዶም ላይ፣
የመፈራረሷን ገመድ፣
የመጥፊያዋንም ቱንቢ ይዘረጋል::
[12]መሳፍንቷም መንግሥት ተብለው ለመጠራት
የሚያስችላቸው ነገር አይኖራቸውም፤
አለቆቿም በሙሉ ጥርግ ብለው ይጠፋሉ::
[13]በቅጥር የተመሸጉ ከተሞቿን እሾኽ፣
ምሽጎቿንም ሳማና አሜከላ ይወርሳቸዋል፤
የቀበሮዎች ጕድጓድ፣
የጕጕቶችም መኖሪያ ትሆናለች::

33፥24 ዘኍ23፥21፤ 2ዜና6፥21፤ኢሳ30፥26፤ 43፥1፤ 48፥20፤ ኤር31፥34፤33፥8፤ 1ዮሐ1፥7-9
34፥1 ዘዳ4፥26፤ መዝ24፥1፤49፥1፤ ኢሳ33፥13፤41፥1፤ 43፥9
34፥2 ኢሳ10፥25፤ 13፥5፤30፥25፤ዘካ5፥3
34፥3 ቍ7፤ 2ሳሙ1፥22፤ መዝ110፥6፤ ኢሳ5፥25፤10፥4፤ 63፥6፤ሕዝ5፥17፤ 14፥19፤32፥6፤35፥6፤ 38፥22፤39፥11፤ ኢዩ2፥20፤አሞ4፥10
34፥4 ኢዮ8፥12፤ 9፥7፤ኢሳ13፥13፤15፥6፤ 38፥12፤ማቴ21፥19፤ 24፥29፤ማር13፥25፤ ዕብ1፥12፤2ጴጥ3፥10
34፥5 ዘዳ13፥15፤ 32፥41-42፤ኢሱ6፥17፤ 2ሳሙ8፥13-14፤ 2ዜና28፥17፤ ኢሳ24፥6፤ኤር47፥6፤ ሕዝ21፥5፤አሞ1፥11-12፤ 3፥14-15፤6፥11፤ ዘካ13፥7፤ሚል1፥4
34፥6 ዘፍ36፥33፤ ዘሌ3፥9፤ዘዳ32፥41፤ ኢሳ27፥1፤30፥25፤ ኤር25፥34፤ራእ19፥17
34፥7 ዘኍ23፥22፤ 2ሳሙ1፥22፤መዝ68፥30
34፥8 ኢሳ1፥24፤ 2፥12፤35፥4፤47፥3፤ 59፥18፤63፥4፤ ሕዝ25፥12-17፤ ኢዩ3፥4፤አሞ1፥6-8፡ 9-10
34፥9 ዘፍ19፥24
34፥10 ቍ17፤ ኢሳ1፥31፤13፥20፤ 24፥1፤ኤር49፥18፤ሕዝ29፥12፤35፥3፤ሚል1፥3፤ራእ14፥10-11፤19፥3
34፥11 ዘፍ1፥2፤8፥7፤ዘሌ11፥16-18፤ ዘዳ14፥15-17፤2ነገ21፥13፤ ኢሳ21፥11፤ሕዝ35፥15፤ኢዩ3፥19፤ አሞ7፥8፤አብ1፥1፤ሚል1፥4፤ ራእ18፥2
34፥12 ኢዮ12፥21፤ መዝ107፥40፤ኢሳ29፥20፤ 40፥23፤41፥11-12፤ኤር21፥7፤27፥20፤ 39፥6፤ሕዝ24፥5
34፥13 ዘሌ11፥16-18፤መዝ44፥19፤ኢሳ5፥6፤7፥19፤13፥22፤ ኤር9፥11፤10፥22

[a]2 በዚህና በቍጥር 5 ላይ የዕብራይስጡ ቃል አንድን ሰው ወይም ነገር ሙሉ በሙሉ በማጥፋት ለእግዚአብሔር መስጠትን የሚያመለክት ነው::
[b]11 የእነዚህ እዕዋፍ ትክክለኛ ማንነታቸው በትክክል አይታወቅም::

እግዚአብሔር የአሦርን ጦር በሚመታበት ጊዜ ማለት ነው (10፥33-34፤ 37፥36 ይመ):: *ምርኮ፤* ቍ 4 ይመ::

*33፥24፤* ከኢሳይያስ ዘመን በኋላ በቍ 17:20-22 እንደ ተገለጸችው በአካልም በመንፈስም ፍጹም የሆነችውን ኢየሩ ሳሌምን የሚያመለክት ነው::

*34፥1-35፥10፤* 34-35 ምዕራፎች፣ የ28-33 ምዕራፎች ማጠ ቃለያ ነው፤ ይህም የምዕራፍ 13-23 ማጠቃለያ የሆነውን የምዕራፍ 24-27ን ሥነ ፍጻሜ ሐሳብ የያዘ ነው (የ24፥1-27፥13 ማብ ይመ)::

34፥2 *ተቈጥቶአል፤ ቍጣውም፤* በጌታ ቀን የሚሆነውን ያመለክታል (2፥11:17:20፤ 26፥20-21 እና ማብ ይመ):: 13፥3 እና ማብ ይመ:: *ፈጽሞ ያጠፋቸዋል፤* በከነዓናውያን ላይ በደረሰው ጥፋት ዐይነት ማለት ነው፤ ቍ 5፤ ኢሱ 6፥17 ይመ:: *ለዕርድም፤* 30፥25 እና ማብ ይመ::

34፥3 *ወደ ውጭ ይጣላሉ፤* ቡተዚቢው ሁኔታ አለመቀበር እንደ ትልቅ ውርደት ይቈጠር ነበር (14፥19 እና ማብ ይመ)::

34፥4 *ከዋክብት ሁሉ ይሟሸሻሉ፤* የጌታ ቀን ሲመጣ በሰ ማያት ታላቅ መናወጥ ይሆናል (13፥10:13 እና ማብ፤ ከሕዝ 32፥7-8 ጋርም ያነጻጽሩ):: *ሰማይ ... ይጠቀለላል ... የከዋክብት ሰራዊት፣* በማቴ 24፥29፤ ራእ 6፥13-14 ተጠቅሶአል:: *ጠውልጎ እንደ ረገፈ የወይን ቅጠል፤* ከ24፥4፤ 40፥7-8 ጋር ያነጻጽሩ::

34፥5 *እስኪበቃት ጠጥታለች፤* ከሕዝ 39፥18-20 ጋር ያነጻጽሩ:: *ኤዶም፤* ስለ ሞዓብ በ25፥10-12 እንደ ተገለጸው፣ የእግዚአብሔርንና የሕዝቡን ጠላቶች በምሳሌ የሚገልጽ ነው፤ የ21፥11 ማብ ይመ:: ምናልባት ከ500 ዓ.ቅ.ክ በፊት ኤዶ ማውያን በነባታውያን ዐረቦች ከአገራቸው ተባርረዋል::

34፥6 *ሥብ፤* ከሥጋ ሁሉ የተሻለ ነው ተብሎ ስለሚታመን፣ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ሆኖ ይቀርብ ነበር (ዘሌ 3፥9-11 ይመ):: *በበግ ጠቦትና በፍየል፤* ሕዝቡን ይወክላል:: *መሥዋዕት፤* ጦርነት አብዛኛውን ጊዜ ከመሥዋዕት ጋር ይነጻጸራል (ኤር 46፥10፤ 50፥27፤ ሕዝ 39፥17-19 ይመ):: *ባሶራ፤* የታወቀች የኤዶም ከተ ማና የበግ አገር ናት:: ከሙት ባሕር ደቡባዊ ጫፍ በስተ ደቡብ ምሥራቅ 40 ኪ.ሜ ላይ ትገኛለች:: ባሶራ ማለትም፣ "ወይን መሰብሰብ" ማለት ነው (ከ63፥1-3 ጋር ያነጻጽሩ)::

34፥7 *ጐሽ... ኮርማም፤* የአሕዛብን ወታደሮች ወይም መሪዎቻ ቸውን ለማመልከት የገባ ነው:: *በደም ትርሳለች፤* ቍ 3 ይመ::

34፥8 *የበቀል ቀን፤* 35፥4፤ 61፥2 ይመ:: ኤዶማውያን እስ ራኤላውያንን በማንኛውም አጋጣሚ ሁሉ ይቃወሟቸው ነበር (2ሳሙ 8፥13-14 ይመ)፤ ኢየሩሳሌምም በተደመሰሰች ጊዜ እጅግ ደስ ብሎአቸው ነበር (ሰቆ 4፥21፤ መዝ 137፥7):: ይሁን እንጂ የኤዶምም ቀን እንዲሁ ቀርቦ ነበር (63፥4 ይመ)::

34፥9 *የሚቃጠል ድኝ፤* የኤዶም መፈራረስ ከሰዶምና ከገሞራ መውደቅ ጋር ተነጻጽሮአል (ኤር 49፥17-18 ይመ)፤ 1፥31 እና ማብ፤ ዘፍ 19፥24 እና ማብ ይመ::

34፥10 *ጢሷም ለዘላለም፤* ይህ አባባል በራእ 19፥3 ላይ ባቢሎንን በተመለከተ ተጠቅሶአል (ራእ 14፥10-11 ይመ):: *ባድማ፤* 13፥20-22 እና ማብ፤ ሚል 1፥3-4 ይመ::

34፥11 *ጭልፊትና ጃርት ... ጕጕትና ቍራም፤* ርኩስ የሆኑ ወፎች ናቸው (ዘዳ 14፥14-17 ይመ):: እንዲህ ዐይነቶቹ ወፎች በባቢሎንና (13፥21) በነነዌ (ሶፎ 2፥14) ከተሞች ፍርስራሽ ውስጥ ይኖራሉ:: *ገመድ ... ቱንቢ፤* 28፥17 እና ማብ ይመ:: *የመፈራረሰዋን ... የመጥፊያዋንም፤* የዕብራይስጡ ትርጕም በዘፍ 1፥2 ላይ ስለ መሬት የተገለጸውን፣ "ምድርም ባዶ ነበረች ቅርጽም አልነበራትም" ከሚለው ጋር አንድ ዐይነት ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)፤ ኤር 4፥23 እና ማብ ይመ::

34፥13 *እሾኽ ... ሳማና አሜከላ፤* ከ7፥24-25 ጋር ያነጻጽሩ::

[14]የምድረ በዳ አራዊት ከጅቦች ጋር አብረው
ይሆናሉ፤
በበረሓ ፍየል የሚመስሉ አጋንንትም እርስ
በእርስ ይጠራራሉ፤
የሌሊት ፍጥረታት ማረፊያቸውን በዚያ
ያደርጋሉ፤
ለራሳቸውም የማረፊያ ቦታ ያገኛሉ።
[15]ጉጉት በዚያ ጉጆ ሠርታ ዕንቍላል ትጥላለች፤
ትቀፈቅፋለች፤ ጫጩቶቿን በክንፎቿ
ትታቀፋቸዋለች፤
ጭላቶችም ጥንድ ጥንድ ሆነው፣
ለርቢ በዚያ ይሰበሰባሉ።

[16]*በእግዚአብሔር* መጽሐፍ እንዲህ የሚለውን
ተመልከቱ፤ አንብቡም፤
ከእነዚህ አንዱ አይጐድልም፤
እያንዳንዷም አጣማጇን አታጣም፤
ይህ ትእዛዝ ከአፉ ወጥቶአል፤
መንፈሱ በአንድ ላይ ይሰበስባቸዋልና።
[17]ድርሻ ድርሻቸውን ይመድብላቸዋል፤
እጁም ለክታ ታካፍላቸዋለች።
ለዘላለም የእነርሱ ትሆናለች፤
ከትውልድ እስከ ትውልድም ይኖሩባታል።

## የተቤዡ ሕዝብ ደስታ

**35** ምድረ በዳውና ደረቁ ምድር ደስ
ይላቸዋል፤
በረሓው ሐሤት ያደርጋል፤ ይፈካል፤
እንደ አደይም ያብባል።
[2]በደስታና በዝማሬ ሐሤት ያደርጋል፤
የሊባኖስ ክብር ይሰጠዋል፤
የቀርሜሎስንና የሳሮንን ግርማ ይለብሳል።
የአምላካችንን ታላቅ ግርማ፣
*የእግዚአብሔርን* ክብር ያያሉ።
[3]የደከሙትን እጆች አበርቱ፤
የላሉትንም ጒልበቶች አጽኑ፤
[4]የሚፈራ ልብ ላላቸው እንዲህ በሉ፤
"በርቱ፤ አትፍሩ፤
አምላካችሁ ይመጣል፤
ሊበቀል ይመጣል፤
እርሱም ብድራቱን ይዞ፣
ሊያድናችሁ ይመጣል።"

[5]በዚያን ጊዜም የዕውር ዐይኖች ይገለጣሉ፤
የደንቈሮም ጆሮዎች ይከፈታሉ።
[6]አንካሳ እንደ ሚዳቋ ይዘላል፤
የድዳውም አንደበት በደስታ ይዘምራል፤
ውሃ ከበረሓ ይወጣል፤
ምንጮችም ከምድረ በዳ ይፈልቃሉ።
[7]ንዳዳማው ምድር ኵሬ ይሆናል፤
የተጠማው መሬት ውሃ ያመነጫል።
ቀበሮዎች በተኙባቸው ጒድጓዶች፣
ሣር፣ ሸምበቆና ደንገል ይበቅልበታል።

[8]በዚያ አውራ ጐዳና ይሆናል፤
"የተቀደሰ መንገድ" ተብሎ ይጠራል።
የረከሱ አይሄዱበትም፤
በመንገዱ ላይ ላሉት ብቻ ይሆናል።
ገራገሮችም ከመንገዱ አይስቱም።
[9]አንበሳ አይኖርበትም፤
ነጣቂ አውሬም አይወጣበትም፤
እነዚህማ በዚያ ስፍራ አይገኙም፤
የዳኑት ብቻ በዚያ ይሄዳሉ፤
[10]*እግዚአብሔር* የዋጃቸው ይመለሳሉ።
እየዘመሩ ወደ ጽዮን ይገባሉ፤
ዘላለማዊ ደስታን እንደ አክሊል ይቀዳጁታል፤
ፍሥሓና ሐሤት ያገኛሉ፤
ሐዘንና ትካዜ ከዚያ ይሸሻሉ።

34፥14 መዝ74፥14፤ ኢሳ13፥22፤ራእ18፥2
34፥15 ዘዳ14፥13፤ መዝ17፥8
34፥16 ኢሳ1፥20፤ 30፥8፤40፥26፤48፥13፤ 58፥14
34፥17 ቍ10፤ ኢሳ17፥14፤ኤር13፥25
35፥1 መሓ2፥11፤ ኢሳ27፥6፡10፤32፥15፡ 16፤41፥18-19፤51፥3
35፥2 ዘኍ21፥6፤ ዘዐ16፥7፤1ዜና27፥29፤ ዕንባ3፥7፤መዝ105፥43፤ መሓ7፥5፤ኢሳ4፥5፤ 12፥6፤25፥9፤33፥9፤ 44፥23፤ 51፥11፤ 52፥9፤55፥12፤59፥19፤ 65፥10
35፥3 ኢዮ4፥4፤ ዕብ12፥12
35፥4 ዘዳ20፥3፤ ኢሱ1፥9፤2ዜና32፥6፤ ኢሳ1፥24፤7፥4፤21፥4፤ 25፥9፤34፥8፤40፥2፡9፡ 10-11፤51፥5፤62፥11፤ ዳን10፥19፤ዘካ1፥13፤ ራእ22፥12
35፥5 መዝ146፥8፤ ኢሳ29፥18፤42፥18፤ 50፥4፤ሐሥ26፥18፤ ዮሐ9፥6-7
35፥6 ዘፀ17፥6፤ 2ሳሙ22፥34፤ መዝ20፥5፤ኢሳ32፥4፤ ማቴ9፥32-33፤ 12፥22፤15፥30፤ ማር7፥35፤ሉቃ7፥22፤ 11፥14፤ዮሐ5፥8-9፤ 7፥38፤ሐሥ3፥8
35፥7 ኢዮ8፥11፤ 40፥21፤መዝ68፥6፤ 107፥35፤ኢሳ13፥22፤ 41፥17፤44፥3፤49፥10፤ 55፥1፤58፥11
35፥8 ኢሳ4፥3፤ 11፥16፤33፥8፤52፥1፤
ኤር31፥21፤ማቴ7፥13-14፤ 1ጴጥ1፥15 35፥9 ዘፀ6፥6፤ ዘሌ25፥47-55፤ ኢሳ11፥6፤13፥22፤30፥6፤34፥14፤51፥11፤ 62፥12፤63፥4 35፥10 ኢዮ19፥25፤ መዝ4፥7፤51፥8፤126፥5፤ ኢሳ1፥27፤25፥9፤30፥19፡29፤51፥3፤ራእ7፥17፤ 21፥4

34፥14 *የምድረ በዳ አራዊት ከጅቦች፤* 13፥21-22 ይመ። *በበረሓ ፍየል፤* አጋንንትን ለማመልከት የገባ ሊሆን ይችላል (የ13፥21 ማብ ይመ)። *የሌሊት ፍጥረታት፤* ከመጽሐፍ ውጭ በሆነ አነጋገር፣ "የሌሊት አጋንንትን" የሚያመለክት ሴማዊ ቃል ነው።

34፥15 *ጉጉት...ጭላቶችም፤* በአረት ሥርዐት መሠረት የረከሱ ወፎች ናቸው (ቍ 11 እና ማብ፤ ዘዳ 14፥13፡15-17 ይመ)።

34፥16 *መጽሐፍ፤* ኤዶም ከተደመሰሰች በኋላ፣ ሕዝቡ ኢሳይያስ የሰጣቸውን ይህን የትንቢት ቃል ያነባሉ። *ከእነዚህ፤* ከላይ የተጠቀሱትን ፍጥረታት ያመለክታል።

34፥17 *ድርሻ ድርሻቸውን ይመድብላቸዋል፤* በቍ 11፡13-15 ለተጠቀሱት ፍጥረታት እግዚአብሔር በቸርነቱ የሚሰጣቸውን ያመለክታል፤ ይህም የኤዶም ምድር ዕጣ ፈንታ ምን እንደሆነ ያሳያል።

35፥1 *ምድረ በዳውና ... ደስ ይላቸዋል፤* በትንቢተ ኢሳይያስ ተፈጥሮን በሰውኛ ዘይቤ መግለጽ የተለመደ ነው። (33፥9፤ 44፥23፤ 55፥12 ይመ)። *በረሓው፤* ዐረባን ለማመልከት ነው (የ33፥9 ማብ ይመ) *አደይ፤* ጽጌረዳ አበባ መሰል ነው (የማሕ 2፥1 ማብ ይመ)።

35፥2 *በደስታና ... ሐሤት ያደርጋል፤* 54፥1 ይመ። *የሊባኖስ ... ቀርሜሎስንና የሳሮንን፤* በልምላሜያቸውና ውብ በሆኑ ዛፎቻቸው የታወቁ ለም ቦታዎች ናቸው (የ33፥9 ማብ ይመ)። *የእግዚአብሔርን ክብር፤* ከፍ ብሎ የተነገረው ታላቅ የተፈጥሮ ለውጥ የተገለጠበትን ያመለክታል።

35፥4 *በርቱ፤ አትፍሩ፤* በኢሱ 1፥6-7፡18 ላይ እግዚአብሔር ለኢያሱ ከሰጠው የማበረታቻ ቃል ጋር ያነጻጽሩ። *አምላካችሁ ይመጣል፤* ስለ ሚመጣው መሲሕ ተመሳሳይ አገላለጽ ጥቅም ላይ ውሎአል (62፥11 ይመ፤ ከራእ 22፥12 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሊበቀል ... ብድራቱን፤* የ34፥8 ማብ ይመ።

35፥5 *ዐይኖች ... ጆሮዎች፤* 29፥18፤ 32፥3፤ 42፥7 እና ማብ ይመ። መንፈሳዊና ሥጋዊ ፈውስ በክርስቶስ አገልግሎት ውስጥም ተካተዋል (ማቴ 11፥5 ይመ)።

35፥6 *አንካሳ ...ይዘላል፤ የዲዳውም አንደበት ...ይዘምራል፤* የመሲሑ ዘመን ምልክቶች ናቸው (ማቴ 12፥22፤ሐሥ 3፥7-8 ይመ)። *ውሃ ... ምንጮችም፤* 32፥2 እና ማብ ይመ፤ እግዚአብሔር ከዐለት አፍልቆ ለሕዝቡ ውሃ ከሰጠበት ከዘፀ 17፥6፤ 2ነገ 3፥15-20 ጋር ያነጻጽሩ።

35፥7 *ውሃ ያመነጫል፤* ከ41፥18 ጋር ያነጻጽሩ። *ሸምበቆና ደንገል፤* በረግረግና እንደ ጣና ባሉ ሐይቆች ዳር የሚበቅሉ ናቸው (ከ19፥6-7 ጋር ያነጻጽሩ)።

35፥8 *አውራ ጐዳና፤* እንደ ልብ መጓጓዝ እንዲቻል ተስተካክሉ የሚሠራ መንገድ (11፥16፤ 40፥3 እና ማብ ይመ)። *የተቀደሰ መንገድ፤* ቅዱሳን ለሆኑ ብቻ የተለየ፣ የዳኑ ብቻ የሚሄዱበት መንገድ (ቍ 9)። በጥንት ዘመን፣ በቤተ መቅደሶች መካከል የሚሠሩ ሥርዐቱ በሚያዘው መሠረት የነጹ ሰዎች የሚተላለፉባቸው መንገዶች ነበሩ።

35፥9 *አንበሳ ... ነጣቂ አውሬም፤* አንዳንድ ጊዜ የዱር አራዊት በመንገደኞች ላይ አደጋ ያደርሱ ነበር (ዘዳ 8፥15፤ መሳ 14፥5 ይመ)። *የዳኑት፤* እግዚአብሔር ከባርነት አገዛዝ ነጻ ያወጣቸው ማለት ነው (ከ1፥27፤51፥10፤ 62፥12፤ ዘሌ 25፥47-48፤ ዘዳ 7፥8 ጋር ያነጻጽሩ)።

*35፥10፤* በ51፥11 ላይ ተደጋግሞአል። *እየዘመሩ ወደ ጽዮን ይገባሉ፤* እስራኤላውያን ከባቢሎን ምርኮ በተመለሱ ጊዜ እንዳደረጉት ማለት ነው (መዝ 126 ይመ)። *ያገኛሉ፤* የሚከታተሏቸው የዱር አራዊት ሳይሆኑ (ቍ 9) ፍሥሓና ሐሤት ያገኛቸዋል ማለት ነው (ከመዝ 23፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሐዘንና ... ይሸሻሉ፤* ከ25፥8፤ 65፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

## የሰናክሬም ዛቻ በኢየሩሳሌም ላይ

**36** ንጉሥ ሕዝቅያስ በነገሠ በዐሥራ አራተኛው ዓመት፣ የአሦር ንጉሥ ሰናክሬም የተመሸጉትን የይሁዳ ከተሞች ሁሉ አጥቅቶ ያዛቸው። [2]የአሦርም ንጉሥ የጦር አዛዡን ከብዙ ሰራዊት ጋር ከለኪሶ፣ ንጉሡ ሕዝቅያስ ወዳለበት፣ ወደ ኢየሩሳሌም ላከው። የጦር አዛዡም ወደ ልብስ አጣቢው ዕርሻ በሚወስደው መንገድ፣ በላይኛው ኵሬ ቦይ አጠገብ ደርሶ ቆመ፤ [3]የቤተ መንግሥቱ አስተዳዳሪ፣ የኬልቅያስ ልጅ ኤልያቄም፣ ጸሓፊው ሳምናስ፣ ታሪክ መዝጋቢውም የአሳፍ ልጅ ዮአስ ወደ እርሱ ወጡ።

[4]የጦር አዛዡም እንዲህ አላቸው፤
"ለሕዝቅያስ እንዲህ ብላችሁ ንገሩት፤

" 'ታላቁ ንጉሥ የአሦር ንጉሥ እንዲህ ይላል፤ እስከዚህ የተማመንህበት ነገር ምንድን ነው? [5]የጦር ስልትና ጠንካራ ሰራዊት አለኝ ትላለህ፤ ነገር ግን ፍሬ ቢስ ቃል ብቻ ትናገራለህ። ለመሆኑ፣ በእኔ ላይ ያመፅኸው በማን ተማምነህ ነው? [6]እነሆ፤ ሰው ሲመረኰዘው እጅ ወግቶ በሚያቈስለው፣ በተሰነጠቀ ሸምበቆ በግብፅ ተማምነሃል፤ የግብፅ ንጉሥ፣ ፈርዖንም ለሚታመኑበት ሁሉ እንዲሁ ነው። [7]ደግሞም፣ "በአምላካችን *በእግዚአብሔር* እንታመናለን" የምትለኝ ከሆነ፣ የእርሱንማ ማምለኪያ ኰረብቶችና መሠዊያዎች ሕዝቅያስ አፍርሶበት ለይሁዳና ለኢየሩሳሌም፣ 'እናንተ መስገድ ያለባችሁ እንዲህ ባለው በአንዱ መሠዊያ ፊት ብቻ ነው" ብሎ የለምን?

[8]" 'አሁን፣ ናና፣ ከጌታዬ ከአሦር ንጉሥ ጋር ተደራደር፤ የሚቀመጡባቸው ሰዎች ካሉህ፣ ሁለት ሺህ ፈረሶች እሰጥሃለሁ። [9]እንግዲህ በግብፅ ሠረገሎችና ፈረሰኞች የምትተማመን ከሆነ፣ ከጌታዬ መኰንንኖች አንዱን ዝቅተኛ መኰንን እንዴት መመለስ ይቻልሃል? [10]ደግሞስ ይህን ምድር ለማጥቃትና ለማጥፋት የመጣሁት ያለ *እግዚአብሔር* ትእዛዝ ይመስልሃልን? *እግዚአብሔር* ራሱ በዚህ አገር ላይ ዘምቼ እንዳጠፋው ነግሮኛል።' "

[11]ኤልያቄምና ሳምናስ እንዲሁም ዮአስ የጦር አዛዡን፣ "እባክህ በምናውቀው በሶርያ ቋንቋ ለባሪያዎችህ ተናገረን፤ በቅጥሩ ላይ ያለው ሕዝብ በሚያውቀው በዕብራይስጥ ቋንቋ አትናገረን" አሉት።

[12]ነገር ግን የጦር አዛዡ መልሶ፣ "ጌታዬ እነዚህን ነገሮች እንድናገር የላከኝ ለጌታህና ለአንተ ብቻ ነበርን? እንደ እናንተ የራሳቸውን ኵስ ለመብላትና ሽንታቸውንም ለመጠጣት በቅጥሩ ላይ ለተቀመጡት ሰዎችም አይደለምን?" አላቸው።

[13]የጦር አዛዡም ቆሞ በዕብራይስጥ ቋንቋ በታላቅ ድምፅ እንዲህ አለ፤ "የታላቁን ንጉሥ፣ የአሦርን ንጉሥ ቃል ስሙ። [14]ንጉሡ እንዲህ ይላል፤ 'ሕዝቅያስ አያታልላችሁ፤ እርሱ ሊያድናችሁም አይችልም። [15]"*እግዚአብሔር* በእርግጥ ያድነናል፤ ይህች ከተማ ለአሦር አትሰጥም" እያለ ሕዝቅያስ *በእግዚአብሔር* እንድትታመኑ አያድርጋችሁ።'

[16]"ሕዝቅያስን አትስሙ። የአሦር ንጉሥ እንዲህ ይላችኋል፤ 'ከእኔ ጋር ተስማሙ፤

36፥1 2ነገ18፥9፤ 2ዜና32፥1፤ መዝ109፥11
36፥2 ኢሱ10፥3፤ ኢሳ7፥3
36፥3 ቍ11፤ ዘፍ41፥40፤2ሳሙ8፥16፡17፤2ነገ18፥18፤ ኢሳ22፥20፡20-21፤ 37፥2
36፥5 2ነገ18፥7
36፥6 2ነገ17፥4፤ ኢሳ8፥12፤30፥2፡5፤ 42፥3፤58፥5፤ ሕዝ17፥17፤29፥6-7
36፥7 ዘዳ12፥2-5፤ 2ነገ18፥4፤2ዜና31፥1፤ መዝ22፥8፤ማቴ27፥43
36፥8 መዝ20፥7፤ ኢሳ30፥16
36፥9 መዝ20፥7፤ ኢሳ30፥2-5፤31፥3፤ 37፥24
36፥10 1ነገ13፥18፤ ኢሳ10፥5-7
36፥11 ቍ3፤ዕዝ4፥7
36፥12 ነገ6፥25፤ ሕዝ4፥12
36፥13 2ዜና32፥18፤ ኢሳ37፥4
36፥14 2ዜና32፥15
36፥15 መዝ3፥2፡7፤ ኢሳ37፥10
36፥16 1ነገ4፥25፤ ምሳ5፥15

*36፥1-39፥8፤* በምዕራፍ 36-39 ጋር በሚጐዳኝ ነው፤ አንዳንድ ጊዜም በ2ነገ 18፥13-20፥19 ያለው ቃል በቃል ተጠቅሶአል። የሁለተኛ ነገሥትን መጽሐፍ የጻፈው በምዕራፍ 36-39 ኢሳይያስ ያለውን ምንጭ በማድረግ ሊሆን ይችላል፤ ወይም ሁለቱም መጻሕፍት ምንጭ ያደረጉት አንድ ሌላ መጽሐፍ ሊኖር ይችላል። ከምዕራፍ 36-37 ያለው ክፍል ስለ አሦር መውደቅ የተነገረውን ትንቢት ፍጻሜ ሲያመለክት፣ ከምዕራፍ 38-39 ያለው ክፍል ደግሞ ስለ ባቢሎን የሚናገረውን፣ በምዕራፍ 40-66 ላይ የሚገኘውን ያመለክታል።

36፥1 *ሕዝቅያስ በነገሠ በዐሥራ አራተኛው ዓመት፤* 701 ዓ.ቅ.ክ ማለት ነው። ሕዝቅያስ ብቻውን ንጉሥ ሆኖ የገዛው 715 - 688ዓ.ቅ.ክ ነበር፤ ይሁን እንጂ በግምት ከ729 ዓ.ቅ.ክ ጀምሮ ከአባቱ ከአካዝ ጋር አገሪቱን ይመራ ነበር (የ2ነገ 18፥1 ማብ ይመ)። *ሰናክሬም፤* 705-681 ዓ.ቅ.ክ አሦርን ገዛ። *ከተሞች ሁሉ፤* ሰናክሬም በታሪክ መጽሐፉ እነዚህን የመሳሰሉ የ46 ከተሞች ዝርዝር አቅርቦአል (የ2ነገ 18፥13 ማብ ይመ)።

36፥2 *ከብዙ ሰራዊት፤* ከ37፥36 ጋር ያነጻጽሩ። *ለኪሶ፤* ከኢየሩሳሌም በስተ ደቡብ ምዕራብ 48 ኪሎ ሜትር ያህል የሚርቅና የይሁዳን ዋና ከተማ በጥብቅ ለመከላከል የሚያስችል ቦታ ነው (ኤር 34፥7 ይመ)። *ዕርሻ ... በላይኛው ኵሬ፤* 7፥3 እና ማብ ይመ፤ የ2ነገ 18፥17 ማብ ይመ።

36፥3 *ኤልያቄም፤* 22፥20-21 እና ማብ ይመ። *የቤተ መንግሥቱ አስተዳዳሪ፤* የቤተ መንግሥቱ አዛዥ ነበር ማለት ነው (22፥15 እና ማብ ይመ)። *ሳምናስ፤* 22፥15 እና ማብ ይመ። *ጸሓፊው፤* ከመንግሥት ዋና ጸሓፊ ጋር እኩል የሆነ ሥልጣን ሳይኖረው አይቀርም (ኤር 36፥12፤ የ2ሳሙ 8፥17 ማብ ይመ)። *ታሪክ መዝጋቢውም፤* በሌላ ስፍራ በጸሓፊነት ደረጃ ከዋና ጸሓፊነት ሥልጣን ጋር ተያይዞ ቀርቦአል (1ነገ 4፥3 ይመ)፤ የ2ሳሙ 8፥16 ማብ ይመ።

36፥4፡13 *ታላቁ ... ንጉሥ፤* የ2ነገ 18፥19 ማብ ይመ።

36፥5 *ያመፅኸው፤* ማግባት የሚገባውን ግብር ባለ ማግባቱ ነው (2ነገ 17፥4፤ 18፥7 ይመ)።

36፥6 በግብፅ፤ በ715 ዓ.ቅ.ክ ወይም ከዚያ በፊት፣ ሕዝቅያስ ከግብፅ ጋር ስምምነት ለማድረግ ያስብ ነበር (20፥5፤ 30፥1 እና ማብ ይመ)። *በተሰነጠቀ ሸምበቆ፤* ግብፅ እንደ ዥና በሕዝ 29፥6-7 ላይ ከተሰነጠቀ ሸምበቆ ጋር ተነጻጽራለች። *ፈርዖንም ... እንዲሁ ነው፤* ከ30፥3፡7 ጋር ያነጻጽሩ።

36፥7 *ማምለኪያ ኰረብቶችና መሠዊያዎች፤* ሕዝቅያስ ለአምልኮ ተሠርተው የነበሩትን አብያተ ጣዖታት በሙሉ አጥፍቶ ነበር (2ነገ 18፥4፤ 2ዜና 31፥1 ይመ)። *መሠዊያዎች፤* በሰሎሞን ቤተ መቅደስ ውስጥ ያሉትን ነው።

36፥8 *ሁለት ሺህ ፈረሶች፤* የአንድ ሰራዊት የተወሰነ ቍጥር፣ ቍጥሩ በአንድ ሰራዊት ክፍል ውስጥ በአነስተኛነት የሚታይ አይደለም። በዚያ ጊዜ ፈረስና ሠረገላ ጠቀሜታቸው እጅግ ከፍ ያለ ነበር (የ30፥16 ማብ ይመ)። *የሚቀመጡባቸው ሰዎች ካገኘህ፤* የ2ነገ 18፥23 ማብ ይመ። *የሚቀመጡባቸው፤* በዚያን ዘመን የተደራጀ ፈረሰኛ ሰራዊት ስላልነበረ፣ ሠረገላ ሳቢ የሆኑትን ሰዎች ሳይመለከት አይቀርም (ቍ 9 ይመ)።

36፥10 *እግዚአብሔር ... ነግሮኛል፤* እግዚአብሔር እስራኤልን ለመቅጣት አሦራውያንን መምቻ በትር አድርጎ ተጠቅሞባቸዋል (10፥5-6 ይመ)፤ አሁን ግን የፍርዱ ቅጣት ባለተራ አሦር ነው። በ2ዜና 35፥21 ላይ እንደ ተጠቀሰው ፈርዖን ኒካው በእግዚአብሔር ፈቃድ የተላከ መሆኑን ተናግሮአል።

36፥11 *ኤልያቄምና ... ዮአስ፤* ቍ 3 እና ማብ ይመ። *በሶርያ ቋንቋ፤* በዚያን ዘመን የአራማይክ ቋንቋ የመንግሥታት መገናኛ ቋንቋ ነበር (የ2ነገ 18፥26 ማብ ይመ)። *በዕብራይስጥ ቋንቋ አትናገረን፤* የእስራኤል ሹማምንት የአሦር መልእክተኛ ንግግር የሕዝቡን ስሜት ሊጐዳ ይችላል ብለው ስለ ፈሩ ነው።

36፥12 *ኵስ መብላትና ሽንታቸውንም ለመጠጣት፤* ኢየሩሳሌም ስትከበብ የሚመጣውን ራብ አስከፊነት ለመግለጥ የገባ አስፈሪ ቃል ነው (ከ2ነገ 6፥25 ጋር ያነጻጽሩ) ከቍ 16 ጋር ያስተያዩ።

36፥14 *አያታልላችሁ፤* ከ37፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

ወደ እኔም ውጡ:: ከዚያም እያንዳንዳችሁ ከወይናችሁና ከበለሳችሁ ትበላላችሁ፤ ከጕድጓዳችሁም ውሃ ትጠጣላችሁ፤ [17]ይኸውም መጥቼ የእህልና የአዲስ ወይን ጠጅ ምድር ወደ ሆነችው፣ የእንጀራና የወይን ምድር ወደ ሆነችው፣ ምድራችሁን ወደምትመስል አገር እስካፈልሳችሁ ድረስ ነው::'

[18]"ሕዝቅያስ፣ 'እግዚአብሔር ያድነናል' በማለት አያታልላችሁ፤ ለመሆኑ፣ እስካሁን ምድሩን ከአሦር ንጉሥ እጅ ያዳነ የየትኛው ሕዝብ አምላክ ነው:: [19]የሐማትና የአርፋድ አማልክት የት አሉ? የሴፈርዋይም አማልክትስ የት አሉ? እነዚህ ሰማርያን ከእጄ አድነዋታልን? [20]ከእነዚህ አገሮች አማልክት ሁሉ፣ ምድሩን ከእጄ ለማዳን የቻለ የትኛው ነው? ታዲያ፣ እግዚአብሔር እንዴት ኢየሩሳሌምን ከእጄ ሊያድን ይችላል?"

[21]ሕዝቡ ግን ንጉሡ፣ "መልስ አትስጡት" ብሎ አዞ ስለ ነበር፣ ዝም አሉ፤ አንዳችም አልመለሱለትም::

[22]የቤተ መንግሥት አስተዳዳሪ የነበረው የኬልቅያስ ልጅ ኤልያቄም፣ ጸሓፊው ሳምናስ፣ ታሪክ መዝጋቢው የአሳፍ ልጅ ዮአስ ልብሳቸውን ቀደው ወደ ሕዝቅያስ መጡ፤ የጦር አዛዡ የተናገረውንም ሁሉ ነገሩት::

## የኢየሩሳሌም ዐርነት ታወጀ

**37** ንጉሡ ሕዝቅያስ ይህን ሲሰማ፣ ልብሱን ቀደደ፤ ማቅ ለበሰ፤ ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ገባ:: [2]የቤተ መንግሥቱን አስተዳዳሪ ኤልያቄምንና ጸሓፊውን ሳምናስ እንዲሁም ከካህናቱ ዋና ዋናዎቹን ማቅ ለብሰው ሁሉም ወደ አሞጽ ልጅ ወደ ነቢዩ ኢሳይያስ እንዲሄዱ ላካቸው:: [3]እነርሱም እንዲህ አሉት፤ "ሕዝቅያስ እንዲህ ይላል፤ ይህ ቀን የጭንቀት፣ የተግሣጽና የውርደት ቀን ነው፤ ሕፃናት ሊወለዱ ሲሉ ብርታት እንደሚታጣበት ቀን ሆኖአል:: [4]ሕያው አምላክን ይገዳደር ዘንድ ጌታው የአሦር ንጉሥ የላከውን የጦር አዛዡን ቃል እግዚአብሔር አምላክህ ይሰማ ይሆናል፤ እግዚአብሔር አምላክህም ሰምቶ ይገሥጸው ይሆናል፤ ስለዚህ አንተም በሕይወት ለተረፉት ቅሬታዎች ጸልይ::"

[5]የንጉሡ የሕዝቅያስ መልእክተኞች ወደ ኢሳይያስ መጡ፤ [6]ኢሳይያስም እንዲህ አላቸው፤ "ጌታችሁን እንዲህ በሉት፤ 'እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ የአሦር ንጉሥ ባሪያዎች እኔን ስለ ሰደቡኝ፣ በሰማኸው ቃል አትሸበር:: [7]እነሆ፤ በላዩ መንፈስን እሰዳለሁ፤ ወሬም ሰምቶ ወደ አገሩ ይመለሳል፤ በዚያ አገሩም በሰይፍ እንዲወድቅ አደርጋለሁ::'"

[8]የጦር አዛዡም፣ የአሦር ንጉሥ ለኪሶን ለቆ መሄዱን ሲሰማ፣ ከነበረበት ተመለሰ፤ ንጉሡም የልብናን ከተማ ሲወጋ አገኘው::

[9]ደግሞም ሰናክሬም፣ የኢትዮጵያ ንጉሥ ቲርሐቅ ሊወጋው መምጣቱን ሰማ፤ ይህንንም እንደ ሰማ ወደ ሕዝቅያስ መልእክተኞች ላከ፤ እንዲህም አለ፤ [10]"ለይሁዳ ንጉሥ ለሕዝቅያስ እንዲህ በሉት፤ 'ኢየሩሳሌም በአሦር ንጉሥ አትያዝም' ብሎ የተማመንህበት አምላክ አያታልህ:: [11]እነሆ፤ የአሦር ነገሥታት በአገሮች ሁሉ ላይ ያደረጉትን፣ ፈጽሞም እንዳጠፏቸው ሰምተሃል፤ አንተስ የምታመልጥ ይመስልሃልን? [12]የቀደሙት አባቶቼ ያጠፏቸውን፣ የጎዛንን፣ የካራንን፣ የራፌስን እንዲሁም በተላሳር የሚኖሩ የዔድንን ሰዎች የአሕዛብ አማልክት አድነዋቸ

36፥17 ዘፍ27፥28፤ ዘዳ28፥51፤2ነገ15፥29
36፥19 2ነገ15፥29፤ 17፥24፤18፥34
36፥20 ዘፀ5፥2፤ 1ነገ20፥23፤ 2ዜና25፥15፤ ኢሳ10፥8-11፤ 37፥10-13፡18-20፤ 40፥18፤ዳን3፥15
36፥21 ምሳ9፥7-8፤ 26፥4
36፥22 ዘፍ37፥29፤ 2ሳሙ8፥16፤ 2ነገ18፥18፤2ዜና34፥19
37፥1 ቍ14፤ ዘፍ37፥29፡34፤ 1ነገ8፥33፤2ዜና34፥19፤ ማቴ21፥13
37፥2 ቍ21፤ 2ነገ18፥18፤ኢሳ1፥1፤ 13፥1፤36፥3፤38፥1
37፥3 መሳ6፥2፤ ኢሳ5፥30፤26፥18፤ 66፥9፤ሆሴ13፥13
37፥4 ቍ23-24፤ ኢሱ3፥10፤1ሳሙ7፥8፤ 2ዜና32፥17፤ኢሳ1፥9፤ 36፥13፡18-20፤አሞ7፥2
37፥6 ዘኍ15፥30፤ ኢሱ1፥9፤ኢሳ7፥4
37፥7 ቍ9፤ 1ዜና5፥26፤ኢሳ31፥8
37፥8 ዘኍ33፥20፤ ኢሱ10፥3
37፥9 ቍ7፤ 2ዜና32፥1፤ኢሳ20፥3
37፥10 2ዜና32፥11፡ 15፤ኢሳ36፥15
37፥11 ኢሳ36፥18-20
37፥12 ዘፍ11፥31፤ 12፥1-4፤2ነገ18፥11፤ ሕዝ27፥23፤አሞ1፥5፤ ሐሥ7፥2

36፥16 *ከወይናችሁና ከበለሳችሁ፤* አገር አማን በሚሆንበት ጊዜ የሰላምና የብልጽግና ምልክቶች ናቸው (1ነገ 4፥25፤ ሚክ 4፥4 ይመ)::

36፥17 *መጥቼ ... እስካፈልሳችሁ፤* አሦራውያን የሚያምፁባቸውን ኀይል ለመቀነስ ሕዝብን ከአንድ ቦታ ወደ ሌላ ቦታ ያዘዋውሩ ነበር (2ዜና 15፥29፤ 17፥6 ይመ):: *የእህልና የአዲስ ወይን ጠጅ፤* ከመደበኛው የእስራኤላውያን ምግብ መካከል ሁለቱ (ከዘፀ 28፥51፤ ሐጌ 1፥11 ጋር ያነጻጽሩ)::

*36፥18-20፤* የአሦር መልእክተኞች የጕራ ንግግር በ10፥8-11 የተጠቀሰውን የአሦራውያንን ትዕቢት ያንጸባርቃል::

36፥19 *የሐማትና የአርፋድ፤* 10፥9 እና ማብ ይመ:: *ሴፈርዋይም፤* ምናልባት ከሐማት ብዙም ሳይርቅ በሰሜን ሶርያ የሚገኝ ስፍራ ሳይሆን አይቀርም:: የሴፈርዋይም ነዋሪዎች በዚያን ጊዜ አድራማሌክንና አናማሌክን ቢያመልኩም እንኳ፣ ወደ ሰማርያ ከመፍለስ አልዳኑም ነበር፤ 2ነገ 17፥24፡31 ይመ:: *ሰማርያ፤* አሦራውያን እያንዳንዱ ሕዝብ የራሱ አምላክ ይኖረዋል ብለው ስለሚያስቡ፣ የይሁዳ አምላክ የሰማርያም አምላክ መሆኑን አላወቁም ነበር::

36፥21 *ሕዝቡ ... ዝም አሉ፤* አሦራውያን የይሁዳን ሕዝብ በንጉሡና በአምላኩ ላይ እንዲያምፁ በቍ 4-20 ላይ ያደረጉት የቅስቀሳ ንግግር አልተሳካም::

*36፥22፤* ቍ 3 እና ማብ ይመ:: *ልብሳቸውን ቀደው፤* የ2ነገ 18፥37 ማብ ይመ::

37፥1 *ልብሱን ... ማቅ፤* ዘፍ 37፥34 እና ማብ ይመ፤ የ2ነገ 18፥37 ማብ ይመ:: *ቤተ መቅደስ፤* የጸሎት ቤት እንዲሆን በሰሎሞን የተመረጠ ቦታ (1ነገ 8፥33 ይመ):: ሕዝቅያስ በእግዚአብሔር ስለ መታመኑ አሦራውያን የተናገሩት (36፥7፡15፡18) እውነት ነበር፤

37፥2 *ኤልያቄም ... ሳምናስ፤* የ36፥3 ማብ ይመ:: *ከካህናቱ ዋና ዋናዎቹ፤* የ2ነገ 19፥2 ማብ ይመ:: *ወደ አሞጽ ልጅ ... ኢሳይያስ፤* የ1፥1 ማብ ይመ:: ነቢያት፣ ካህናትና ነገሥታት በአንድነት ወደ እግዚአብሔር የምልጃ ጸሎት ያቀርቡ ነበር::

37፥3 *ይህ ቀን የጭንቀት፤* 5፥30፤ 26፥16፤ 33፥2 እና ማብ ይመ:: *ሕፃናት ሊወለዱ ሲሉ፤* ከምጥ ጣር የበለጠ የጭንቅ ጊዜን የሚያመለክት ነው (13፥8 እና ማብ ይመ)::

37፥4 *ይገዳደር ዘንድ፤* በዕብራይስጡ "ይሳደብ ዘንድ" እንደ ማለት ነው (ቍ 17፡23-24 ይመ):: *ቅሬታዎች፤* ኢየሩሳሌም ሰው አልባ ሆና ቀርታለች (36፥1 እና የ1፥9፤ 2ነገ 19፥4 ማብ እንደዚሁም 10፥20-22 ይመ):: *ጸልይ፤* የ2ነገ 19፥4 ማብ ይመ::

37፥6 *አትሸበር፤* ከ7፥4 ጋር ያነጻጽሩ፤ 35፥4 እና ማብ ይመ::

37፥7 *መንፈስን፤* ምናልባት እንዲመለሱ የሚያስገድድ ወይም እንዲዘጋጁ የሚያደርግ (ከ1ዜና 5፥26 ጋር ያነጻጽሩ):: *ወሬም፤* የ2ነገ 19፥7 ማብ ይመ:: *ይመለሳል ... በሰይፍ እንዲወድቅ አደርጋለሁ፤* ቍ 37-38 ይመ::

37፥8 *ለኪሶን፤* የ36፥2 ማብ ይመ:: *የልብናን፤* የ2ነገ 8፥22 ማብ፤ ኢሱ 10፥31 ይመ::

37፥9 *የኢትዮጵያ ንጉሥ ቲርሐቅ፤* በ701 ዓ.ቅ.ክ ላይ መስፍን ነበር (የአዲሱ ፈርዖን የሸቢትኩ ወንድም ሲሆን፣ ሕዝቅያስ አሦራውያንን መቋቋም እንዲችል ፈርዖኑ ከወታደሮች ጋር ልኮት ነበር)፤ ስለዚህ እስከ 690 ዓ.ቅ.ክ ድረስ በትረ መንግሥት አልጨበጠም ነበር:: ይሁን እንጂ ይህ የኢሳይያስ መጽሐፍ ክፍል ከ681 ዓ.ቅ.ክ በፊት ስላልተጻፈ (የቍ 38 ማብ ይመ)፣ ቲርሐቅ የኢትዮጵያ ንጉሥ ተብሎ መጠቀሱ ትክክል ነው፤ 18፥1 እና ማብ ይመ::

37፥10 *አምላክ አያታልህ፤* 36፥14-15፡18 ይመ:: የቍ 10-13 መልእክት ከ36፡18-20 ጋር ተመሳሳይ ነው (በዚያኑ ማብ ይመ)::

37፥12 *ጎዛን፤* ከመስጴጦምያ በስተ ሰሜን በኩል የነበረ፣ አሦራውያን የተወሰኑ እስራኤላውያንን አግዘው ያኖሩበት ከተማ ነው (2ነገ 17፥6 ይመ):: *ካራን፤* ለብዙ ዓመት አብርሃም የኖረበት ከጎዛን በስተ ምዕራብ የሚገኝ ከተማ (ዘፍ 11፥31 እና ማብ ይመ):: *ራፌስ፤* በኤፍራጥስ ወንዝና በካራን መካከል ያለ ከተማ:: *ዔድን፤* በኤፍራጥስና በባሊክ

ዋልን? [13]የሐማት ንጉሥ፣ የአርፋድ ንጉሥ፣ የሴፈርዋይም ከተማ ንጉሥ፣ የሄና ንጉሥ ወይም የዒዋ ንጉሥ የት አሉ?"

## የሕዝቅያስ ጸሎት

[14]ሕዝቅያስ ደብዳቤውን ከመልእክተኞቹ ተቀብሎ አነበበው፤ ወደ *እግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ወጥቶም ደብዳቤውን *በእግዚአብሔር* ፊት ዘረጋው። [15]ሕዝቅያስም እንዲህ ሲል ወደ *እግዚአብሔር* ጸለየ፤ [16]"በኪሩቤል ላይ የምት ቀመጥ፣ የእስራኤል አምላክ፣ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ በምድር ባሉ መንግሥታት ሁሉ ላይ አንተ ብቻ አምላክ ነህ፤ ሰማይንና ምድርንም ፈጥረሃል። [17]አቤቱ፣ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ጆሮህን አዘንብል፤ አድምጥም። *እግዚአ ብሔር* ሆይ፤ ዐይኖችህን ክፈት፤ ተመልከትም። ሰናክሬም ሕያው ስሙባክን ለመሳደብ የላከውን ቃል ስማ።

[18]"*እግዚአብሔር* ሆይ፤ በእርግጥ የአሦር ነገሥታት እነዚህን ሕዝቦች፣ ምድራቸውንም ሁሉ ባድማ አድርገዋል። [19]አማልክታቸውን ወደ እሳት ጥለዋል፤ በሰው እጅ የተቀረጹ የድንጋይና የዕንጨት ምስሎች እንጂ አማልክት አልነበሩምና። [20]አሁንም፣ *እግዚአብሔር* ስሙባ ካችን ሆይ፤ የምድር መንግሥታት ሁሉ አንተ *እግዚአብሔር* ብቻ አምላክ እንደ ሆንህ ያውቁ ዘንድ፣ አቤቱ ከእጁ አድነን።"

## የሰናክሬም ውድቀት

[21]ከዚህ በኋላ የአሞጽ ልጅ ኢሳይያስ እንዲህ የሚል መልእክት ወደ ሕዝቅያስ ላከ፤ "የእስ ራኤል ስሙባክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ስለ አሦር ንጉሥ፣ ስለ ሰናክሬም ወደ እኔ ጸልየሃልና፣ [22]*እግዚአብሔር* በእርሱ ላይ የተናገረው ቃል ይህ ነው፤

" 'ድንግሊቱ የጽዮን ልጅ፣
 ንቃሃለች፣ አፌዛብሃለች፤
የኢየሩሳሌም ልጅ፣
 አንተ ስትሸሽ ራሷን ነቅንቃብሃለች።
[23]የሰደብኸውና ያቃለልኸው ማንን ነው?
 ድምፅህንስ ከፍ ከፍ ያደረግኸው፣
ዐይንህን በትዕቢት ያነሣኸው በማን ላይ ነው?
 በእስራኤል ቅዱስ ላይ ነው እኮ!
[24]በመልእክተኞችህ በኩል፣
 በጌታ ላይ ብዙ የስድብ ቃል ተናገርህ፤
እንዲህም አልህ፤
 "በሠረገሎቼ ብዛት፣
የተራሮችንም ከፍታ፣
 የሊባኖስንም ጫፍ ወጥቻለሁ፤
ረጃጅም ዝግባዎችን፣
 የተመረጡ ጥዶችን ቈርጫለሁ፤
እጅግ ወደራቁት ከፍታዎች፣
 እጅግ ውብ ወደ ሆኑትም ደኖች
  ደርሻለሁ፤
[25]በባዕድ ምድር* ጕድጓዶችን ቈፈርሁ፤
 ከዚያም ውሃ ጠጣሁ።
የግብፅን ምንጮች ሁሉ፣
 በእግሬ ረግጬ አደረቅሁ።"
[26]" 'ይህን ቀድሞ እንደ ወሰንሁት፣
 ጥንትም እንዳቀድሁት፣
አልሰማህምን?
 አሁን ደግሞ እንዲፈጸም አደረግሁት፤
 አንተም የተመሸጉትን ከተሞች የድንጋይ
  ክምር አደረግሃቸው።
[27]የሕዝቦቻቸው ኀይል ተሟጦአል፤
 ደንግጠዋል፤ ተዋርደዋልም፤
በሜዳ እንዳሉ ዕፀዋት፣
 እንደ ለጋ ቡቃያ፣
በሰገነት ላይ እንደ በቀለ ሣር፣
 በእንጭጩ ዋግ እንደ መታው ሆነዋል።
[28]" 'እኔ ግን የት እንዳለህ፣
 መምጣት መሄድህ ምን ጊዜ እንደ ሆነ፣
 በእኔም ላይ እንዴት በቍጣ እንደም
  ትነሣሣ ዐውቃለሁ።
[29]በእኔ ላይ በቍጣ ስለ ተነሣሣህ፣
 እብሪትህም ወደ ጆሮዬ ስለ ደረሰ፣

37፥13 2ነገ17፥24፤ ኢሳ10፥9፤36፥20
37፥14 ቍ1:38፤ 1ነገ8፥33፤2ዜና32፥17
37፥15 2ዜና32፥20
37፥16 ዘፍ1፥1፤ 3፥24፤ዘጸ10፥17፤ መዝ2፥4፤46፥10፤ 86፥10፤136፥2-3፤ ኢሳ11፥12፤41፥9፤ 43፥6፤ዳን4፥34፤ ሐሥ4፥24
37፥17 ኢሱ3፥10፤ 1ነገ8፥29፤2ዜና6፥40፤ 32፥1:17፤ኤር25፥29፤ ዳን9፥18
37፥18 2ነገ15፥29፤ ናሆ2፥11-12
37፥19 ኢሱ7፥15፤ 2ዜና13፥9፤ 2ዜና32፥19፤ መዝ135፥15፤ ኢሳ26፥14፤ 36፥20፤40፥17:18-20፤ 41፥24:29፤44፥9-11፤ ኤር2፥11፤5፥7፤ 16፥20፤ገላ4፥8
37፥20 ኢሱ4፥24፤ 1ሳሙ17፥46፤ መዝ3፥2:7፤46፥10፤ ምሳ20፥22
37፥21 ቍ2
37፥22 ኢዮ16፥4፤ ኢሳ10፥32፤23፥12
37፥23 ቍ4፤ ዘኍ15፥30፤ኢዮ15፥25፤ ኢሳ1፥4፤2፥11፤12፥6፤ 52፥5፤ሕዝ36፥20:23፤ ዳን7፥25
37፥24 1ነገ5፥8-10፤ 7፥2፤ኢሳ14፥8:13፤ 33፥9፤36፥9፤41፥19፤ 55፥13፤60፥13፤ ሆሴ14፥8
37፥25 ዘጸ11፥10፤ ኢሳ10፥14፤19፥6፤ 44፥27፤ዳን4፥30
37፥26 ዘጸ13፥16፤ ኢሳ10፥6፤25፥1:2፤ ሐሥ2፥23፤4፥27-28፤ 1ጴጥ2፥8
37፥27 መዝ129፥6፤ ኢሳ15፥6
37፥28 መዝ2፥1፤ 139፥1-3
37፥29 ቍ34፤ 2ዜና33፥11፤ኢዮ40፥24፤ኢሳ10፥12

*25 የሙት ባሕር ቅጆች (እንዲሁም 2 ነገ 19፥24 ይመ) ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ *በባዕድ ምድር* የሚለውን ሐረግ አይጨምርም።

ወንዝ መካከል ያለ የቢት አድኒ መንግሥት ነው (የ2ነገ 19፥12 ማብ ይመ)።

37፥13 *የሐማት ... የአርፋድ፤* 10፥9 እና ማብ ይመ። *ሴፈርዋይም፤* 36፥19 እና ማብ ይመ።

37፥14 *ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፤* ቍ 1 እና ማብ ይመ። *ዘረጋው፤* በ1፥15 ላይ በግብዝነት እጅን ዘርግቶ መጸለይ በእግዚአብሔር ዘንድ ተቀባይነት እንደ ሌለው ከተገለጸበት ሁኔታ ጋር ይህን ያነጻጽሩ።

37፥16 *በኪሩቤል ላይ የምትቀመጥ፤* 1ሳሙ 4፥4 እና ማብ ይመ። *የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 13፥4 እና ማብ ይመ። *መንግሥታት ሁሉ፤* ከ40፥17 ጋር ያነጻጽሩ። *ሰማይንና ምድርንም ፈጥረሃል፤* የእግዚአብሔር ፈጣሪነት በ40፥26:28፤ 42፥5፤ 45፥12 ላይ በአጽንዖት ተገልጾአል።

37፥17 *ጆሮህን አዘንብል ... ዐይኖችህን ክፈት፤* በ1ነገ 8፥52፤ 2ዜና 6፥40 ላይ ሰሎሞን ከጸለየው ጸሎት ጋር ያነጻጽሩ። *ሕያው አምላክን ለመሳደብ፤* ቍ 4 እና ማብ ይመ።

37፥19 *የድንጋይና የዕንጨት፤* ከ2፥8፤ 44፥9-10 ጋር ያነጻጽሩ። *አማልክት አልነበሩምና፤* 36፥19 እና ማብ ይመ።

37፥20 *አንተ ... ብቻ አምላክ እንደ ሆንህ፤* ከ43፥11፤ 45፥18:21-22 ጋር ያነጻጽሩ።

37፥22 *ድንግሊቱ የጽዮን ልጅ፤* ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን በሰውኛ ዘይቤ ለመግለጽ የገባ ቃል ነው። *ራሷን ነቅንቃብሃለች፤* የፌዝ አገላለጽ (መዝ 22፥7፤ 44፥14 ይመ)

37፥23 *በትዕቢት ያነሣኸው፤* ቀደም ብሎ የአሦር ትዕቢት ተወግዞ ነበር (10፥12 እና ማብ ይመ)። *በእስራኤል ቅዱስ፤* ኢሳይያስ ብዙውን ጊዜ የእስራኤልን አምላክ ለመግለጽ የሚጠቀምበት አባባል ነው (1፥4 እና ማብ ይመ)።

37፥24 *በሠረገሎቼ ብዛት፤* 36፥8 እና ማብ ይመ። *ተራ ሮች ከፍታ፤* በ14፥13-14 ከተገለጸው ከባቢሎን ንጉሥ አነጋገር ጋር ያነጻጽሩ። *ሊባኖስ፤* 33፥9፤ 35፥2 እና ማብ ይመ። *ዝግባዎችን ... ቈርጫለሁ፤* ለብዙ ዘመን የመስጴጦምያ ነገሥታት የቤተ መንግሥት ሕንጻን ለመሥራት በሊባኖስ ዝግባዎች ተጠቅመዋል (ከ1ነገ 5፥8-10 ጋር ያነጻጽሩ)።

37፥25 *ጕድጓዶችን ቈፈርሁ፤* ምድረ በዳው አላገደውም ማለት ነው። *ምንጮች ሁሉ ... አደረቅሁ፤* የዐባይ ወንዝ ግብሮችን ዕንቅፋት አልሆኑም ነበር፤ እንዲህ ዐይነቱ አባባል ራስን እንደ አምላክ አድርጎ እንደ ማየት ያስቈጥራል 11፥15፤ የ44፥27 ማብ ይመ።

*37፥26፤* ከ40፥21 ጋር ያነጻጽሩ። *ከተሞች የድንጋይ ክምር፤* አሦር እግዚአብሔር ሌሎች መንግሥታትን የሚቀጣበት መሣሪያ ነበር (10፥5-6 ይመ)።

*37፥27፤* 40፥6-8፤ መዝ 37፥1-2 ይመ። *በሰገነት ላይ ... ሣር፤* በመካከለኛው ምሥራቅ ባሉ አገሮች የሚሠሩ ቤቶች ጣራ ቸው ጠፍጣፋ ነው።

በአፍንጫህ ስናጌን፣
በአፍህ ልጓሜን አገባለሁ፤
በመጣህበትም መንገድ እንድትመለስ
አደርግሃለሁ።’

[30]“ሕዝቅያስ ሆይ፤ ይህ ምልክት ይሆንልሃል፤

“በዚህ ዓመት የገበውን፣
በሚቀጥለው ዓመት ከገበው የበቀለውን
ትበላላችሁ፤
በሦስተኛው ዓመት ግን ትዘራላችሁ፤
ታጭዳላችሁ፤
ወይን ትተክላላችሁ፤ ፍሬውንም ትበላላችሁ።
[31]እንደ ገናም የይሁዳ ቤት ቅሬታ፣
ሥሩን ወደ ታች ይሰዳል፤ ከላይም ፍሬ
ያፈራል፤
[32]ቅሬታ የሆኑት ከኢየሩሳሌም፣
የተረፉትም ከጽዮን ተራራ ይመጣሉና፤
የሰራዊት ጌታ *የእግዚአብሔር* ቅናት
ይህን ያደርጋል።

[33]“ስለዚህ *እግዚአብሔር* ስለ አሦር ንጉሥ
እንዲህ ይላል፤
“ወደዚች ከተማ አይገባም፤
ፍላጻ አይወረውርባትም፤
ጋሻ አንግቦ አይመጣባትም፤
በዐፈር ቍልልም አይከባትም።
[34]በመጣበት መንገድ ይመለሳል፤
ወደዚች ከተማም አይገባም”
ይላል *እግዚአብሔር*።

[35]“ስለ ራሴና፣ ስለ አገልጋዬም ስለ ዳዊት፣
ይህችን ከተማ እጋርዳታለሁ፤ አድናታለሁም።”

[36]ከዚያም *የእግዚአብሔር* መልአክ ወጣ፤ ከአሦራውያን ሰፈር አንድ መቶ ሰማንያ አምስት ሺህ ሰው ገደለ፤ በሰፈር ያሉት ማለዳ ሲነሡ፣ በታው ሬሳ በሬሳ ነበር። [37]ስለዚህ የአሦር ንጉሥ ሰናክሬም አመለጠ፤ ወደ ነነዌም ተመልሶ በዚያ ተቀመጠ። [38]ሰናክሬም በአምላኩ በናሳራክ ቤት ጣዖት በሚሰግድበት ጊዜ፣ ልጆቹ አድራሜሌክና ሳራሳር በሰይፍ ገደሉት፤ ከዚያም ወደ አራራት ምድር ኰበለሉ፤ ልጁም አስራዶን በምትኩ ነገሠ።

37፥30 ዘሌ25፥4፤ መዝ107፥37፤ ኢሳ16፥14፤20፥31 30፥23፤32፥10፤ 65፥21፤ኤር31፥5
37፥31 ኢሳ11፥10፤ 27፥6
37፥32 ኢሳ1፥9፤ 9፥7፤11፥11
37፥33 2ሳሙ20፥15፤ ኢሳ32፥18
37፥34 ቍ29
37፥35 1ዜና17፥19፤ ኢሳ31፥5፤43፥25፤ 48፥9፡11፤ ሕዝ36፥21-22
37፥36 ዘፀ12፥12፡23፤ ኢሳ10፥12
37፥37 ዘፍ10፥11፤ 2ዜና32፥1፤ናሆ1፥1
37፥38 ቍ14፤ ዘፍ8፥4፤2ነገ17፥24፤ ኢሳ9፥4፤10፥26፤ 14፥25፤ኤር51፥27
38፥1 2ሳሙ17፥23፤ 2ነገ8፥10፤ኢሳ37፥2
38፥3 ዘዳ6፥18፤ 10፥20፤1ነገ8፥61፤ 1ዜና29፥19፤ መዝ6፥8፤26፥3
38፥4 1ሳሙ13፥13፤ ኢሳ39፥5
38፥5 2ነገ18፥2፡3፤ መዝ6፥6
38፥6 ኢሳ31፥5
38፥7 ዘፍ24፥14፤ 2ዜና32፥31፤ ኢሳ7፥11፡14፤20፥3
38፥8 ኢሱ10፥13
38፥10 እዮ17፥11፡16፤ መዝ102፥24፤

## የሕዝቅያስ መታመም

**38** በዚያ ጊዜ ሕዝቅያስ ታመመ፤ ሞት አፋፍ ደረሰ፤ የአሞጽ ልጅ ነቢዩ ኢሳይያስም ወደ እርሱ መጥቶ፣ “*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ‘ከሕመምህ አትድንም፤ ትሞታለህና ቤትህን አስናዳ’ ” አለው።

[2]ሕዝቅያስም ፊቱን ወደ ግድግዳ አዙሮ፣ እንዲህ ሲል ወደ *እግዚአብሔር* ጸለየ፤ [3]“*እግዚአብሔር* ሆይ፤ በፊትህ በታማኝነትና በፍጹም ልብ ደስ የሚያሰኝህንም በማድረግ እንዴት እንደ ኖርሁ አቤቱ አስብ።” ሕዝቅያስም አምርሮ አለቀሰ።

[4]*የእግዚአብሔርም* ቃል ወደ ኢሳይያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [5]“ሂድና ለሕዝቅያስ እንዲህ ብለህ ንገረው፤ ‘የአባትህ የዳዊት አምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ጸሎትህን ሰምቻለሁ፤ እንባህንም አይቻለሁ፤ በዕድሜህም ላይ ዐሥራ አምስት ዓመት እጨምርልሃለሁ። [6]አንተንና ይህቺን ከተማ ከአሦር ንጉሥ እጅ እታደጋለሁ፤ ለከተማዋም እከላከልላታለሁ።

[7]“ ‘*እግዚአብሔር* የገባልህን ቃል እንደሚፈጽምልህ፣ *የእግዚአብሔር* ምልክት ይህ ነው፤ [8]በአካዝ የሰዓት መቍጠሪያ ደረጃ ላይ፣ የወረደውን የፀሓይ ጥላ በዐሥር ደረጃ ወደ ኋላ እንዲመለስ አደርጋለሁ።’ ” ስለዚህ ወርዶ የነበረው የፀሓይ ጥላ ያንኑ ያህል ወደ ኋላ ተመለሰ።
[9]የይሁዳ ንጉሥ ሕዝቅያስ ከሕመሙ ከተፈወሰ
በኋላ የጻፈው ጽሕፈት፤

[10]እኔ፣ “በዕድሜዬ እኩሌታ፣

37፥29 *በአፍንጫህ ስናጌን፤* አሦራውያን ምርኮኞቻቸውን በአፍንጫቸው ላይ ቀለበት በማስገር እርስ በርስ አጠላልፈው በገመድ እየጐተቱ ከቦታ ወደ ቦታ ይዘዋቸው ይሄዱ ነበር (የ2ነገ 19፥28 ማብ ይመ)። *ልጓሜን፤* ከ30፥28 ጋር ያነጻጽሩ።

37፥30 *ምልክት፤* 7፥11፡14 ማብ ይመ። *ከገበው፤* የ2ነገ 19፥29 ማብ ይመ። *በሚቀጥለው ዓመት … በሦሥተኛው ዓመት፤* የ2ነገ 19፥29 ማብ ይመ። ሁለተኛው ዓመት ቶሎ ይጀምር ይሆናል፤ ስለዚህ አጠቃላዩ ጊዜ ከ36 ወራት ያንሳል። ሌላው የሦስተኛው ዓመት ምልክት በ20፥3 ላይ ተጠቅሶአል። *ወይን ትተክላላችሁ፤ ፍሬውንም ትበላላችሁ፤* በ36፥16 ላይ የተገለጸው የአሦር ምላሽ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)።

37፥31-32 *ቅሬታ፤* የቍ 4፤ 1፥9፤ 2ነገ 19፥4፡30-31 ማብ ይመ።

37፥31 *ሥሩን … ይሰዳል፤ ከላይም ፍሬ ያፈራል፤* 4፥2፤ 11፥1፡10፤ 27፥6 እና ማብ ይመ።

37፥32 *ቅናት ይህን፤* 9፥7 እና ማብ ይመ።

37፥33 *በዐፈር ቍልልም፤* ወራሪዎች ዕርድ ሠርተው ቅጥሩን በመክበብ ሕዝቡን ሊያስጨንቁ አይችሉም ማለት ነው (2ሳሙ 20፥15 ይመ)።

37፥35 *ስለ ዳዊት፤* እግዚአብሔር በኢየሩሳሌም ለዳዊት ዘላለማዊ ዘሩን እንደሚሰጠው ቃል ገብቶለታል (9፥7፤ 55፥3፤ 2ሳሙ 7፥16 ይመ)።

37፥36 *የእግዚአብሔርም መልአክ … ገደለ፤* ይህን በግብፅ በኵር በኵሩን ሁሉ ካጠፋውና (ዘፀ 12፥12) በኢየሩሳሌም ላይ ከተሰነዘረው የመልአክ ሰይፍ (2ሳሙ 24፥16) ጋር ያነጻጽሩ። ሄሮዶቱስ የተባለው የግሪክ ታሪክ ጸሓፊ ይህን ጥፋት የቡብኒክ መቅሠፍት ከተባለው ጋር አያይዞታል። የእነዚህ ወታደሮች መገደል በ10፥33-34፤ 30፥31፤ 31፥8 ለተጠቀሰው ትንቢት ፍጻሜ ነው።

37፥37 *ነነዌ፤* የአሦር ዋና ከተማ ናት፤ ዮና 1፥2 ይመ።

37፥38 *በቤተ ጣዖት፤* ሕዝቅያስ ኀይሉን ያጠናከረው ወደ ቤተ መቅደስ በመግባት ነበር (ቍ 1፡14 ይመ)። ከሃያ ዓመት በኋላ በ681 ዓ.ቅ.ክ ላይ ሰናክሬም ወደ አምላኩ ቤት ሄዶ እዚያው ተገደለ። *አራራት፤* በሰሜን አሦር በአርመን ምድር ኡራርቱ የሚባለው ስፍራ ነው (የዘፍ 8፥4 ማብ ይመ)። *አስራዶን፤* የነገሠበት ዘመን ከ681-669 ዓ.ቅ.ክ ላይ ባለው ጊዜ ነበር፤ ዕዝ 4፥2 ይመ።

38፥1 *በዚያን ጊዜ፤* ከሰናክሬም ወረራ በፊት 701 ዓ.ቅ.ክ ላይ ማለት ነው (ቍ6 ይመ)። *ኢሳይያስ፤* በዚህ ታሪካዊ ዘመን እጅግ የታወቀ ሰው ነበር (ከምዕራፍ 36-39)። *ቤትህን አስናዳ፤* የ2ነገ20፥1 ማብ ይመ። *ትሞታለህና፤* ነቢዩ ኤልሳዕም እንዲሁ ወልደ አዴር እንደሚሞት ተናግሮ ነበር (2ነገ8፥9-10)። የ2ነገ20፥1 ማብ ይመ።

38፥2 *ግድግዳ፤* በአቅራቢያው የነበረውን የቤተ መቅደስ የሚመለከት ሳይሆን አይቀርም። *ጸለየ፤* በእግሩ ሊተካ የሚችል የደረሰ ልጅ በወቅቱ ስለ ሌለው ሊሆን ይችላል (ከ39፥7፤ 2ነገ21፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

38፥3 *በፍጹም ልብ፤* እንደ ዳዊት (1ነገ11፥4)፣ ሕዝቅያስ በእርግጥ ታማኝ ሰው ነበረ (36፥7፤ 2ነገ18፥3-5 ይመ)።

38፥6 *ይህቺንም ከተማ … እከላከልላታለሁ፤* 31፥5፤ 37፥35 ይመ።

38፥7 *ምልክት፤* 7፥11፡14 እና ማብ ይመ።

38፥8 *የፀሓይ ጥላ … ወደ ኋላ እንዲመለስ፤* ምናልባት እዚህ ላይ ታምራቱ የፀሓይ ብርሃን ከቦታው ዐሥር ደረጃ ወደ ኋላ መመለስ ነው (2ነገ20፥9-11፤ኢሱ10፥12-14 ይመ)።

*38፥10-20፤* ከብዙ መዝሙሮች ጋር ተመሳሳይ የሆነ የምስጋና

በሲኦል ደጆች ማለፍ አለብኝን?
የቀረውንስ ዘመኔን ልነጠቅ ይገባልን?" አልሁ::
11እንዲህም አልሁ፤ "ዳግም እግዚአብሔርን፣
እግዚአብሔርን በሕያዋን ምድር አላይም፤
ከእንግዲህም የሰውን ዘር አላይም፤
በዚህ ዓለም ከሚኖሩትም ጋር አልሆንም::
12ቤቴ እንደ እረኛ ድንኳን ተነቀለ፤
ከእኔም ተወሰደ፤
ሕይወቴን እንደ ሸማኔ ጠቀለልሁ፤
ከመጠቅለያ ቈርጦኛል፤
ከጠዋት እስከ ማታ ልትጨርሰኝ ፈጠንህ::
13እስከ ማለዳ በትዕግሥት ጠበቅሁ፤
እርሱ ግን እንደ አንበሳ ዐጥንቶቼን ሁሉ ሰባበረ፤
ከጠዋት እስከ ማታም ልትጨርሰኝ ፈጠንህ::
14እንደ ጨረባ፣ እንደ ሽመላም ተንጫጫሁ፤
እንደ ርግብ አልጐመጐምሁ፤
ዐይኖቼ ወደ ሰማይ በመመልከት ደከሙ፤
ጌታ ሆይ፤ ተጨንቄአለሁና ታደገኝ::"

15እንግዲህ ምን እላለሁ?
እርሱ ተናግሮኛል፤ ራሱ ደግሞ ይህን አድርጓል፤
ስለ ነፍሴ ጭንቀት፣
ዕድሜዬን ሁሉ በትሕትና እሄዳለሁ::
16ጌታ ሆይ፤ ሰዎች በእነዚህ ነገሮች ይኖራሉ፤
መንፈሴም እንዲሁ በእነዚህ ሕይወትን ያገኛል፤
ፈወስኸኝ፤
በሕይወትም አኖርኸኝ::
17እነሆ፤ በሥቃይ የተጨነቅሁት፣
ለጥቅሜ ሆነ፤
ከጥፋት ጕድጓድ፣
በፍቅርህ ጠበቅኸኝ፤
ኀጢአቴንም ሁሉ፣
ወደ ኋላህ ጣልኸ::
18ሲኦል አያመሰግንህም፤
ሞት አያወድስህም፤
ወደ ጕድጓድ የሚወርዱ፣
የአንተን ታማኝነት ተስፋ አያደርጉም::
19እኔ ዛሬ እንደማደርገው፣
ሕያዋን እነርሱ ያመሰግኑሃል::
ስለ አንተ ታማኝነትም፣
አባቶች ለልጆቻቸው ይነግራሉ::
20እግዚአብሔር ያድነኛል፤
ስለዚህ በዕድሜ ዘመናችን ሁሉ፣
በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፣
አውታር ባለው መሣሪያ እንዘምራለን::

21ኢሳይያስም፣ "የበለስ ጥፍጥፍ ወስዳችሁ በዕባጩ ላይ አድርጉለት እርሱም ይፈወሳል" ብሎ ነበር::

22ሕዝቅያስም፣ "ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ እወጣ ዘንድ ምልክቱ ምንድን ነው?" ብሎ ነበር::

## ከባቢሎን የመጡ መልእክተኞች

39 በዚያን ጊዜ የባቢሎን ንጉሥ፣ የባልዳን ልጅ፣ መሮዳክ ባልዳን የሕዝቅያስን መታመምና መፈወስ ሰምቶ ስለ ነበር፣ ደብዳቤና ስጦታ ላከለት:: 2ሕዝቅያስም መልእክተኞቹን በደስታ ተቀበለ፤ ለእነርሱም በግምጃ ቤቱ ውስጥ ያለውን ብሩን፣ ወርቁን፣ ቅመማ ቅመሙን፣ ምርጡን ዘይት እንዲሁም የጦር መሣሪያውን በሙሉ፣ ያለውንም ንብረት አንዳች ሳያስቀር አሳያቸው:: በቤተ መንግሥቱም ሆነ በግዛቱ ሁሉ ሕዝቅያስ ያላሳያቸው ነገር አልነበረም::

3ከዚያም ነቢዩ ኢሳይያስ ወደ ንጉሡ ሕዝቅያስ መጥቶ፣ "እነዚያ ሰዎች ምን አሉህ? ወደ

107፥18፤2ቆሮ1፥9
38፥11 ኢዮ28፥13፤ መዝ116፥9፤ኢሳ12፥2
38፥12 ቍ13፤ ዘኍ11፥15፤ኢዮ4፥21፤ 7፥6፤መዝ31፥22፤ 32፥4፤73፥14፤ ኢሳ33፥20፤34፥4፤ 2ቆሮ5፥1፡4፤ ዕብ1፥12፤ 2ጴጥ1፥13-14
38፥13 ቍ12፤ ኢዮ9፥17፤10፥16፤ መዝ37፥7፤51፥8፤ ኤር34፥17፤ሰቆ3፥4፤ ዳን6፥24
38፥14 ዘፍ8፥8፤ 50፥24፤ኢዮ17፥3፤ መዝ6፥7፤ኢሳ59፥11
38፥15 2ሳሙ7፥20፤ 1ነገ21፥27፤ኢዮ7፥11፤ መዝ39፥9
38፥16 መዝ119፥25፤ ዕብ12፥9
38፥17 ኢዮ7፥11፤ 17፥16፤መዝ30፥3፤ 103፥3፡12፤119፥71፡ 75፤ኢሳ43፥25፤ ኤር31፥34፤ ሚክ7፥19፤ ሮሜ8፥28፤ዕብ12፥11
38፥18 ዘኍ16፥30፤ መዝ6፥5፤30፥9፤ 88፥10-11፤115፥17፤ መክ9፥10
38፥19 ዘዳ11፥19፤ መዝ118፥17፤119፥75
38፥20 መዝ23፥6፤ 33፥2፤45፥8፤63፥4፤ 68፥25፤116፥3፡17-19
38፥22 2ዜና32፥31
39፥1 2ዜና32፥31
39፥2 2ነገ18፥15፤ 2ዜና32፥27-29፡31

መዝሙር ነው፤ ይህም ሕዝቅያስ አብዛኛውን የዳዊትንና የአሳፍን መዝሙር ይወድ እንደ ነበር ያመለክታል (2ዜና29፥30 ይመ)::

*38፥10-14፤* ሕዝቅያስ ሐዘኑን የገለጸበት ነው::

38፥11 *እግዚአብሔርን፣ እግዚአብሔርን፤* 26፥4 ይመ:: *በሕያዋን ምድር፤* ከመዝ 27፥13 ጋር ያነጻጽሩ::

38፥12 *ሕይወቴን ... ጠቀለልሁ፤* በ34፥4 ላይ ሰማይ እንደ ጥቅልል መጽሐፍ ከተጠቀለለበት ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ (ዕብ1፥12 ይመ)::

38፥13 *ዐጥንቶቼን ...ሰባበረ፤* የአካል ወይም የመንፈስ ጕዳት ብዙውን ጊዜ በአካል ሕመም ወይም በዐጥንት መሰበር ይገለጻል (መዝ6፥2፤ 32፥3 ይመ)::

*38፥15-20፤* ሕዝቅያስ ስለ ተፈወሰ እግዚአብሔርን ያመሰግናል::

38፥15 *እንግዲህ ምን እላለሁ?* 2ሳሙ7፥20 ይመ:: ሕዝቅያስ እግዚአብሔርን የሚያመሰግንበት ቃል እንዳጠረው ያመለክታል::

38፥16 *በእነዚህ ነገሮች፤* የእግዚአብሔር ቸርነት ሕመምንና ጭንቀትን አጠቃሎ የሚይዝ ቢሆንም፤ ሕዝቅያስ እዚህ ላይ የሚገልጸው የእግዚአብሔርን የተስፋ ቃልና ቸርነት ነው::

38፥17 *ከጥፋት ጕድጓድ፤* መቃብርን የሚያመለክት ነው (መዝ55፥23 ይመ):: *ኀጢአቴንም ሁሉ፤* አንዳንድ ጊዜ መንፈሳዊና ሥጋዊ ፈውስ በአንድነት ሲፈጸም ይታያል (53፥4-5 ይመ):: *ኀጢአቴንም ሁሉ ወደ ኋላህ ጣልኸ፤* እግዚአብሔር ኀጢአታችንን ከፊታችን ማራቅ ብቻ ሳይሆን ወደማይደረስበትም ቦታ ይጥለዋል (ሚክ7፥19፤ መዝ103፥12)፤ ከሐሳባችንም ያወጣዋል (ኤር31፥34)፤ ይደመስሰዋልም (ኢሳ43፥25፤ 44፥22፤ መዝ51፥1፡9፤ ሐሥ 3፥19)::

38፥18 *ተስፋ አያደርጉም፤* በብሉይ ኪዳን ዘመን ከሞት በኋላ ስላለው ሕይወት የሚታወቀው ውሱን ነበር የክርስቶስ ወንጌል ግን፣ "ሕይወትንና አለመጥፋትን ወደ ብርሃን አምጥቶአል" (2ጢሞ 1፥10)::

38፥20 *አውታር ባለው መሣሪያ እንዘምራለን፤* የሙዚቃ መሣሪያና የምስጋና መዝሙር በአምልኮ ጊዜ በአንድነት አገልግሎት መስጠታቸው የተለመደ ነበር (ከመዝ33፥1-3 ጋር ያነጻጽሩ):: *በዕድሜ ዘመናችን ሁሉ በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፤* ልክ እንደ ዳዊት (መዝ 23፥6) ሕዝቅያስም የእግዚአብሔርን ቤት ይወድ ነበር::

38፥21 *ወስዳችሁ ... አድርጉለት፤* ግሱ በብዙ ቍጥር ስለሆነ፣ የቤተ መንግሥቱን ሐኪሞች የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም:: *የበለስ ጥፍጥፍ፤* በጥንታዊቷ ኡጋሪት በለስን በመድኀኒትነት ይጠቀሙበት ነበር:: *ይፈወሳል፤* ከቍ1 ጋር ያስተያዩ:: ሕዝቅያስ እንዲፈወስ ለጸለየው ጸሎት እግዚአብሔር መለሰለት (ቍ5 ይመ)::

38፥22 *ምልክቱ፤* ምናልባት የዕባጩን መፈወስ ለማመልከት ይሆናል (ቍ21 ይመ)::

39፥1 *ባቢሎን፤* የ13፥1 ማብ ይመ:: *መሮዳክ ባልዳን፤* ከ721-710 ዓ.ቅ.ክ እና ከዚያም በኋላ ገዝቶአል (2ነገ20፥12 ማብ ይመ):: *ደብዳቤና ስጦታ ላከለት፤* መሮዳክ ባልዳን ይህን ያደረገው፣ ምናልባት በአሦር ላይ ላቀደው ዘመቻ የሕዝቅያስን ርዳታ ፈልጎ ይሆናል:: ይህን እዳር ለማድረስ በሚጠላቸው በጎረቤቶቹ ላይ የተለያዩ የዐመፅ እንቅስቃሴዎችን ለማካሄድ ዝግጅት አድርጎአል፤ የ2ነገ20፥12 ማብ ይመ::

39፥2 *ብሩን፣ ወርቁን ... ያለውንም ንብረት፤* 2ዜና32፥27-29፡31 ይመ:: ሕዝቅያስ የአሦራውያንን ጥቃት ለመከላከል ምናልባት የባቢሎንን ርዳታ ሳይፈልግ አልቀረም (የ2ነገ20፥13 ማብ ይመ):: ነገር ግን የባቢሎን መልእክተኞች ጕብኝትና የተመለከቱት ነገር ሁሉ ለመሮዳክ ባልዳን ወራሾች ጠቃሚ መረጃ ሳይሆን እንዳልቀረ ይታሰባል (ቍ5-7 ይመ)::

39፥3 *ነቢዩ ኢሳይያስ፤* እግዚአብሔር ቀደም ሲል ኢሳይያስ፣

አንተ ዘንድ የመጡትስ ከየት ነው?" አለው።
ሕዝቅያስም፣ "ወደ እኔ የመጡት ከሩቅ አገር፣ ከባቢሎን ነው" አለው።
[4]ነቢዩም፣ "በቤተ መንግሥትህ ያዩት ምን ድን ነው?" አለው።
ሕዝቅያስም፣ "በቤተ መንግሥቴ ያለውን ሁሉ አይተዋል፤ ከንብረቴ ያላሳየኋቸው ምንም ነገር የለም" አለ።
[5]ኢሳይያስም ሕዝቅያስን እንዲህ አለው፤ "የሰራዊት ጌታ የእግዚአብሔርን ቃል ስማ፤ [6]'እነሆ፤ በቤተ መንግሥትህ ያለው ሁሉ፣ አባቶችህ እስከዚህች ቀን ድረስ ያከማቹትም ሁሉ ወደ ባቢሎን ተማርኮ የሚወሰድበት ቀን ይመጣል፤ አንዳች የሚተርፍ ነገር የለም፤ ይላል እግዚአብሔር። [7]ከአብራክህ ከሚከፈሉት፣ ከዘርህ፣ ከአንተ ከሚወለዱት ልጆች ተወስደው፣ በባቢሎን ንጉሥ ቤተ መንግሥት ጃንደረባዎች ይሆናሉ።' "
[8]ሕዝቅያስም፣ "የተናገርኸው የእግዚአብሔር ቃል መልካም ነው" አለው፤ "በዘመኔ ሰላምና ጸጥታ ከኖረ ዘንድ" ብሎ ዐስቦ ነበርና።

## *የእግዚአብሔርን ሕዝብ የሚያጽናና ቃል*

**40** አጽናኑ፤ ሕዝቤን አጽናኑ፤
ይላል አምላካችሁ።
[2]ለኢየሩሳሌም አለዝባችሁ ንገሯት፤
ዐውጁላትም፤
በባርነት ያገለገለችበት ዘመን አብቅቶአል፤
የኀጢአቷም ዋጋ ተከፍሎአል፤
ስለ ኀጢአቷ ሁሉ ከእግዚአብሔር እጅ
ሁለት ዕጥፍ ተቀብላለች።
[3]የዐዋጅ ነጋሪ ድምፅ እንዲህ ይላል፤
"የእግዚአብሔርን መንገድ፣
በምድረ በዳ አዘጋጁ፤
ለአምላካችን አውራ ጐዳና፣
በበረሓ አስተካክሉ።
[4]ሸለቆው ሁሉ ከፍ ይላል፤
ተራራውና ኰረብታው ሁሉ ዝቅ ይላል፤
ወጣ ገባው ምድር ይስተካከላል፤
ሰርጓጕጡም ሜዳ ይሆናል።
[5]የእግዚአብሔርም ክብር ይገለጣል፤
ሰው ሁሉ በአንድነት ያየዋል፤
የእግዚአብሔር አፍ ይህን ተናግሮአልና።"
[6]ድምፅም፣ "ጩኽ" አለኝ፤
እኔም፣ "ምን ብዬ ልጩኽ?" አልሁ።
"ሰው ሁሉ እንደ ሣር ነው፤
ክብሩም ሁሉ እንደ ሜዳ አበባ ነው።
[7]ሣሩ ይደርቃል፤ አበባውም ይረግፋል፤
የእግዚአብሔር እስትንፋስ ነፍሶበታልና፤
ሕዝቡ በእርግጥ ሣር ነው።
[8]ሣሩ ይደርቃል፤ አበባውም ይረግፋል፤
የአምላካችን ቃል ግን ለዘላለም ጸንቶ ይኖራል።"
[9]አንተ ለጽዮን የምሥራችን የምትነግር፤

39፥3 ዘዳ28፥49
39፥5 ኢሳ38፥4
39፥6 መሳ6፥4፤ 2ነገ24፥13
39፥7 2ነገ24፥15፤ ዳን1፥1-7
39፥8 መሳ10፥15፤ 2ዜና32፥36፤ ኢዮ1፥21፤መዝ39፥9
40፥1 ኢሳ12፥1፤ 49፥13፤51፥3፡12፤ 52፥9፤57፥18፤61፥2፤ 66፥13፤ኤር31፥13፤ ሶፎ3፥14-17፤ ዘካ1፥17፤2ቆሮ1፥3
40፥2 ዘፍ34፥3፤ ዘሌ26፥41፤ኢዮ7፥1፤ ኢሳ35፥4፤41፥11-13፤ 49፥25፤51፥19፤61፥7፤ ኤር16፥18፤17፥18፤ ዘካ9፥12፤ ራእ18፥6
40፥3 ምሳ3፥5-6፤ ኢሳ11፥16፤43፥19፤ ሚል3፥1፤ማቴ3፥3፤ ማር1፥3፤ዮሐ1፥23
40፥4 መዝ26፥12፤ ኢሳ2፥14፤26፥7፤ 45፥2፡13፤49፥11፤ ኤር31፥9
40፥5 ዘፀ16፥7፤ ዘኍ14፥21፤ኢሳ1፥20፤ 52፥10፤58፥14፤ 59፥19፤62፥2፤ ሉቃ2፥30፤3፥4-6
40፥6 ዘፍ6፥3፤ ኢሳ29፥5
40፥7 ዘፀ15፥10፤ ኢዮ8፥12፤41፥21፤ መዝ103፥16፤ ኢሳ15፥6፤ሕዝ22፥21
ምሳ19፥21፤ኢሳ5፥24፤7፥7፡9፤55፥11፤59፥21፤ኤር39፥16፤ማቴ5፥18፤ ያዕ1፥10፤1ጴጥ1፥24-25 40፥9 ኢሳ1፥1፤25፥9፤41፥27፤44፥28፤ 52፥7-10፤61፥1፤ናሆ1፥15፤ሐሥ13፥32፤ሮሜ10፥15፤1ቆሮ15፥1-4

ንጉሥ አካዝን እንዲያገኘው ልኮት ነበር (7፥3)፤ ነቢዩ ናታን ንጉሥ ዳዊትን ከገሠጸበት ሁኔታ (2ሳሙ12፥1፡7) ጋር ይህን ያነጻጽሩ።

39፥5 *የእግዚአብሔርን ቃል፤* በ38፥4-6 የተጠቀሰውን የተስፋ ቃል ከዚህ ጋር ያስተያዩ።

39፥6 *ወደ ባቢሎን ተማርኮ የሚወሰድበት፤* በ14፥3-4 ላይ ስለ ባቢሎን ምርኮ ቢነገርም፣ ባቢሎን ኢየሩሳሌምን እንደምታሸንፍ ሲነገር ይህ የመጀመሪያው ነው። ለምርኮው ዋና ምክንያት የሆነው የሕዝቅያስ ልጅ የምናሴ ክፋት ነበር (2ነገ21፥11-15 ይመ)። የ2ነገ20፥17 ማብ ይመ።

39፥7 *ከዘርህ፤* እንደ ንጉሥ ዮአኪን ያሉትን ነው (2ነገ24፥15)። *ጃንደረባዎች፤* በዕብራይስጥ ይህ ስም ለቤተ መንግሥት ሹማምንት ከተሰጠበት ከዳን 1፥3-6 ጋር ያነጻጽሩ። *በባቢሎን ንጉሥ፤* ናቡከደነፆር ነው።

39፥8 *ቃል መልካም ነው፤* የ2ነገ20፥19 ማብ ይመ። *በዘመኔ ሰላምና፤* 2ነገ22፥20 ይመ። "ሰላም" የሚለው ቃል የመጨረሻዎቹን 27 ምዕራፎች 3 ቦታ ከፍሎ እያንዳንዱን 9 ምዕራፍ በማድረግ በ48፥22፤ 57፥21 ላይ እንደ አዝማች ተጠቅሶአል።

*40፥1-66፥24፤* ነቢዩ ኢሳይያስ ከምዕራፍ 1-35 በይሁዳና በኢየሩሳሌም ላይ ከሚደርሰው ከአሦር ጥቃት በፊት መከላከያ ሊሆን የሚችለውን ነገር በማውሳት ትንቢት የተናገረ ሲሆን፣ ከምዕራፍ 36-39 ደግሞ ስለ አሦር ውድቀት ጽፎአል፤ ባቢሎን ወደፊት ስለ መነሣቷም ማስጠንቀቂያ ሰጥቶአል። በምዕራፍ 40-66 ላይ የይሁዳ በባቢሎን ተማርኮ መኖር እንደሚያበቃ ተናግሮአል።

40፥1 *አጽናኑ ... አጽናኑ፤* "አብዝታችሁ አጽናኑ" ለማለት ተደጋግሞ የተጻፈ ነው። ለአጽንዖት ሲባል በተደጋጋሚ የተጠቀሰው ይህ ቃል በ51፥9፡17፤ 52፥1፡11፤ 57፥14፤ 62፥10 በዚሁ ዐይነት ተጽፎአል።

40፥2 *አለዝባችሁ ንገሯት፤* ይህን ሐረግ የሚተካው የዕብራይስጥ ቃል፣ አሦር ይሁዳን ሊወር ባሰበ ጊዜ ሕዝቡ በእግዚአብሔር እንዲታመን ንጉሡ ሕዝቅያስ፣ "የሚያጽናና" ቃል በተናገረበት በ2ዜና32፥6 ላይ ተጠቅሶአል። *በባርነት ያገለገለችበት፤* በባቢሎን የነበረውን የምርኮ ዘመን አስከፊነት የሚያሳስብ ነው (ከመዝ137፥1-6፤ ኤር1፥1-2፡9፡16-17፡21 ጋር ያነጻጽሩ)። *የኀጢአቷም ዋጋ ተከፍሎአል፤* በምርኮ በቈየችበት ዘመን የተቀበለችውን መከራ ጽናት ለማለት ነው (ዘሌ26፥41 ይመ)። *ዕጥፍ፤* ሙሉ ወይም በቂ ቅጣት አግኝታለች ማለት ነው፤ በ51፥19፣ "ሁለት ጥፋቶች" ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ።

40፥3 *ድምፅ፤* በቍ1 የተጠቀሰው መጽናናት እንዴት እንደሚመጣ ቃሉ ሦስት ጊዜ ተጽፎአል (ቍ3፡6፡9)። በዚህ ቍጥር የተጠቀሰውን ድምፅ፣ አዲስ ኪዳን በማቴ3፥3፤ ማር1፥3፤ ሉቃ3፥4፤ ዮሐ1፥23 ተጽፎ ከሚገኘው ከመጥምቁ ዮሐንስ ጋር ያያይዘዋል። *መንገድ ... አዘጋጁ፤* እንቅፋት የሆኑትን ነገሮች ከመንገድ አስወግዱ ማለት ነው (ከ57፥14፤ 62፥10 ጋር ያነጻጽሩ)። ከቍ3-4 ያለው ቃል የተጠቀሰበት ቋንቋ በጥንት የመካከለኛ ምሥራቅ አገሮች ልማድ፣ ንጉሥ አንዱን ስፍራ ከመጐብኘቱ በፊት መልእክተኞች ሁኔታውን ማመቻቸት እንዳለባቸው የሚያመለክት ሐሳብ ነው። ምሳሌነቱም ጌታ ወደ ኢየሩሳሌም ከመምጣቱ በፊት አውራ ጐዳናው መስተካከል እንዳለበት ያመለክታል። በማቴ3፥1-8 መጥምቁ ዮሐንስ ለክርስትና መንገዱን ለማዘጋጀት ንስሓ መግባት አስፈላጊ እንደ ሆነ ተናግሮአል። *አውራ ጐዳናን ... አስተካክሉ፤* 11፥16፤ 35፥8 እና ማብ ይመ።

40፥4 *ወጣ ገባው ምድር ይስተካከል፤* 26፥7 እና ማብ ይመ።

40፥5 *ክብር ይገለጣል፤* እግዚአብሔር እስራኤልን ከባቢሎን ባርነት ነጻ ያወጣል (35፥2 እና ማብ 44፥23 ይመ)፤ አሕዛብም ሁሉ የእስራኤልን ነጻ መውጣት ያያሉ (52፥10፤ ከሉቃ3፥16 ጋር ያነጻጽሩ)። በመጨረሻ ነጻ የሚያወጣው የእግዚአብሔር ክብር በኢየሱስ ክርስቶስ ይታያል (ዮሐ1፥14፤ 11፥4፡40፤ 17፥4፤ ዕብ1፥3 ይመ)። ይልቁንም ተመልሶ ሲመጣ የበለጠ ይገለጣል (ማቴ16፥27፤ 24፥30፤ 25፥31፤ ራእ1፥7)፤ በዳኑትም ሕይወት ይታያል (1ቆሮ10፥31፤ 2ቆሮ3፥18፤ ኤፌ3፥21 ይመ)፤ ኢሳ6፥3 እና ማብ ይመ።

*40፥6፡8፤* በከፊል በ1ጴጥ1፥24-25 ላይ ተጠቅሶአል።

40፥6 *እንደ ሣር፤* 37፥27 እና ማብ፤ 51፥12 ይመ። *ክብሩም ሁሉ እንደ ሜዳ፤* የአሦርና የባቢሎን ኀይል እንኳ ይጠፋል ለማለት ነው።

40፥8 *የአምላካችን ቃል ግን ... ጸንቶ ይኖራል፤* የአሕዛብ ሐሳብና ዕቅድ ግን አይከናወንም (8፥10 እና ማብ ይመ)።

40፥9 *ለጽዮን የምሥራች፤* እግዚአብሔር ሕዝቡን ወደ ይሁዳ እንደሚመልስ የተነገረውን ቃል የሚመለከት ነው (ቍ10-11)። ሌሕ

ከፍ ወዳለው ተራራ ውጣ፤
አንተ ለኢየሩሳሌም ብሥራት የምትነግር፣[f]
ድምፅህን ከፍ አድርገህ ጩኽ።
ከፍ አድርገው፤ አትፍራ፤
ለይሁዳም ከተሞች፣
"እነሆ፤ አምላካችሁ!" በል።
[10]እነሆ፤ ልዑል እግዚአብሔር በኀይል ይመጣል፤
ክንዱ ስለ እርሱ ይገዛል።
እነሆ፤ ዋጋው ከእርሱ ጋር ነው፤
የሚከፍለውም ብድራት አብሮት አለ።
[11]መንጋውን እንደ እረኛ ያሰማራል፤
ጠቦቶቹን በክንዱ ይሰበስባል፤
በዕቅፉም ይይዛቸዋል፤
የሚያጠቡትንም በጥንቃቄ ይመራል።

[12]ውሆችን በዕፍኙ የሰፈረ፣
ሰማያትን በስንዝሩ የለካ፣
የምድርን ዐፈር በመስፈሪያ ሰብስቦ የያዘ፣
ተራሮችን በሚዛን፣
ኰረብቶችንም በመድሎት የመዘነ ማነው?
[13]*የእግዚአብሔርን መንፈስ የተረዳ፣*
አማካሪውስ ሆኖ ያስተማረው ማነው?
[14]ዕውቀት ለማግኘት እግዚአብሔር ማንን
አማከረ?
ትክክለኛውንስ መንገድ ማን አስተማረው?
ዕውቀትን ያስተማረው፣
የማስተዋልንም መንገድ ያሳየው ማን ነበር?

[15]እነሆ፤ አሕዛብ በገንቦ ውስጥ እንዳለች ጠብታ
ናቸው፤
በሚዛን ላይ እንዳለ ትቢያ ይቈጠራሉ፤
ደሴቶችንም እንደ ደቃቅ ዐፈር
ይመዝናቸዋል።
[16]ሊባኖስ ለመሠዊያ እሳት አትበቃም፤
የእንስሶቿም ቍጥር ለሚቃጠል መሥዋዕት
ያንሳል።
[17]አሕዛብ ሁሉ በፊቱ እንደ ኢምንት ናቸው፤
ከምንም የማይቈጠሩ መና ናቸው።

40፥8 መዝ119፥89፤
40፥10 መዝ44፥3፤ ኢሳ9፥6-7፤28፥21፤ 30፥30፤33፥2፤35፥4፤ 59፥20፤ማቴ21፥5፤ ራእ22፥7:12
40፥11 ዘፍ33፥13፤ 48፥15፤ዘኍ11፥12፤ ዘዳ26፥19፤30፥4፤ መዝ28፥9፤ኢሳ49፥10፤ ሚክ5፥4፤ዮሐ10፥11
40፥12 ኢዮ12፥15፤ 38፥5:10:18፤ ምሳ16፥11፤30፥4፤ ዕብ1፥10-12
40፥13 ኢዮ15፥8፤ ኢሳ11፥2፤42፥1፤ ሮሜ11፥34፤1ቆሮ2፥16
40፥14 ኢዮ12፥13፤ 21፥22፤34፥13፤ ኢሳ55፥9፤ቈላ2፥3
40፥15 ዘዳ9፥21፤ መዝ62፥9፤ኢሳ2፥22
40፥16 መዝ50፥9-11፤ኢሳ33፥9፤37፥24፤ ሚክ6፥7፤ዕብ10፥5-9
40፥17 ኢዮ12፥19፤ ኢሳ29፥7፤30፥28፤ 37፥19፤ዳን4፥35
40፥18 ዘፀ8፥10፤ ዘዳ4፥15፤1ሳሙ2፥2፤ ሐሥ17፥29
40፥19 ዘፀ20፥4፤ መዝ115፥4፤ኢሳ2፥20፤ 31፥7፤37፥19፤41፥7፤ 42፥17፤46፥6፤ ኤር2፥8:28፤10፥3:8፤ 16፥19፤ዕን2፥18፤ ዘካ10፥2
40፥20 1ሳሙ5፥3፤ 12፥21፤ኢሳ44፥19
40፥21 ቍ28፤ ዘፍ1፥1፤2ነገ19፥25፤ መዝ19፥1፤50፥6፤ ኢሳ41፥22፤42፥9፤ 44፥8፤48፥3:5:13፤ 51፥13፤ሐሥ14፥17፤ ሮሜ1፥19
40፥22 ዘፍ1፥1፤ 1፥8፤ዘኍ13፥33፤ 2ዜና6፥18፤ 36፥29፤መዝ2፥4፤ኢሳ48፥13
40፥23 ኢዮ12፥18: 19፤ኢሳ34፥12፤ አሞ2፥3
40፥24 2ሳሙ22፥16፤ኢዮ5፥3፤8፥12፤18፥16፤24፥24፤ኢሳ11፥4፤ 41፥16፤41፥2

[18]እንግዲህ፣ እግዚአብሔርን ከማን ጋር
ታወዳድሩታላችሁ?
ከየትኛውስ ምስል ጋር ታነጻጽሩታላችሁ?
[19]የተቀረጸውንማ ምስል ባለጅ ይቀርጸዋል፤
ወርቅ አንጥረኛም በወርቅ ይለብጠዋል፤
የብር ሰንሰለትም ያበጅለታል።
[20]እንዲህ ያለውን መባ ማቅረብ የማይችል
ምስኪን ድኻ፣
የማይነቅዝ ዕንጨት ይመርጣል፤
የማይወድቅ ምስልን ለማቆምም፣
ታዋቂ ባለሙያ ይፈልጋል።
[21]አላወቃችሁምን?
አልሰማችሁምን?
ከጥንት አልተነገራችሁምን?
ምድር ከተመሠረተች ጀምሮ አላስተዋ
ላችሁምን?
[22]እርሱ ከምድር ክበብ በላይ በዙፋን ላይ
ይቀመጣል፤
ሕዝቦቿም እንደ አንበጣ ናቸው።
ሰማያትን እንደ ድባብ ይዘረጋቸዋል፤
እንደ መኖሪያ ድንኳንም ይተክላቸዋል።
[23]አለቆችን ኢምንት፣
የዚህን ዓለም ገዦች እንዳልነበሩ
ያደርጋቸዋል።
[24]ተተክለው ምንም ያህል ሳይቈዩ፣
ተዘርተው ምንም ያህል ሳይሰነብቱ፣
ገና ሥር መስደድ ሳይጀምሩ
አነፈሰባቸው፤ እነርሱም ደረቁ፤
ዐውሎ ነፋስም እንደ ገለባ ጠራርጎ
ወሰዳቸው።

[f]9 *ወይም፣ ጽዮን ሆይ፤ የምሥራቹን የምታበስሪ፤ ወደ ረጅም ተራራ ላይ ውጪ። የምሥራቹን የምታበስሪ ኢየሩሳሌም ሆይ*

ዝቡ ያስባል፤ ከባርነትም ነጻ ያወጣቸዋል (52፥7-10፤ 61፥1)። አዲስ ኪዳን ይህን የምሥራች ወይም ወንጌል ሰፋ በማድረግ ለሕዝቡ ሁሉ በክርስቶስ በኩል የሚገኘው ድነት ታላቅ ብሥራት እንደ ሆነ ያመለክታል (1ቆሮ15፥1-4)። *እነሆ፤ አምላካችሁ፤* ጌታ ወደ ኢየሩሳሌም ይመለሳል። እነዚህ ቃሎች ከምርኮ መመለስን (52፥7-9)፣ የክርስቶስን የመጀመሪያ ምጽአት (ማቴ21፥5)፣ ደግሞ ምጽአቱን (62፥11፤ ራእ 22፥12) ያመለክታሉ፤ 35፥4 እና ማብ ይመ።

40፥10 *ክንዱ ... ይገዛል፤* ከ51፥9፤59፥16 ጋር ያነጻጽሩ፤ ብርታትና ጥንቃቄ የባሕርዩ ነው (ቍ11)። *ዋጋው ... የሚከፍለውም ብድራት፤* በቍ11 የተጠቀሰው መንጋ፣ ሕዝቡን የሚያመለክት ነው (62፥11-12)።

40፥11 *መንጋውን ... ያሰማራል፤* ከኤር31፥10፤ ሕዝ34፥11-16 ጋር ያነጻጽሩ።

*40፥12-31፤* የተዘረዘሩት መልስ አዘል ጥያቄዎች፣ ማዳን እንዲሁም ሕዝቡን ማበርታትና መመለስ የሚችለውን እግዚአብሔርን እንዲያምኑ የሚያደርጉ ናቸው።

40፥12 *ውሆችን... የሰፈረ፤* ኢዮ28፥25፤ 38፥8 ይመ። በኢዮብ 38-41 እግዚአብሔር ታላቅነቱን በገለጠበት ንግግሩ ኢዮብን እንዳስደነቀው ተጽፎአል። *ሰማያትን ... የለካ፤* 48፥13 ይመ።

*40፥13፤* በሮሜ 11፥34፤ 1ቆሮ2፥16፤ ላይ ተጠቅሶአል። *አማከረ፤* 9፥6 እና ማብ ይመ።

40፥15 *አሕዛብ በገንቦ ውስጥ እንዳለች ጠብታ፤* የቍ6 ማብ ይመ። *ዐፈር፤* 17፥13 እና ማብ 29፥5 ይመ።

40፥16 *ሊባኖስ፤* የዝግባ ዛፎችን ያመለክታል። *የእንስሶቿም፤* ከመዝ104፥16-18 ጋር ያነጻጽሩ። መሥዋዕቶች የቱንም ያህል ቢበዙ፣ ለእግዚአብሔር ታላቅነት የሚያመጡት ምንም ፍትሕ የለም።

40፥17 *ኢምንት ... መና፤* ከሚያሳዩት ጊዜ ያዊ ክብር በቀር ዋጋ የላቸውም ማለት ነው (13፥19 እና ማብ ይመ)።

*40፥18-20፤* ኢሳይያስ ከማንኛውም ነቢይ ይልቅ፣ ጣዖትን ማምለክ ከንቱ እንደ ሆነ ገልጾአል። በአሽሙር፣ በፌዝና በቀልድ ጣዖት አምልኮን ያወገዘበት ቃል ከፍተኛ ደረጃ ላይ የደረሰው በ44፥9-20 ነው (41፥7:22-24፤ 42፥17፤ 46፥5-7፤ 48፥5 ይመ)።

40፥18 *እግዚአብሔርን ከማን ጋር ታወዳድሩታላችሁ?* ቍ25፤ 46፥5 ይመ።

40፥19 *ባለጅ ... ወርቅ አንጥረኛም፤* 41፥7፤ 44፥10-12 ይመ። *ወርቅ ...የብር፤* 2፥20፤ ዕን2፥18-19 እና ማብ ይመ።

40፥20 *ዕንጨት፤* 44፥14-16:19 ይመ። *የማይወድቅ፤* 41፥7፤ 46፥7 ይመ።

40፥21 *ከጥንት፤* በቀሩት ምዕራፎች የእግዚአብሔር ሥራ እንደ ፈጣሪነቱ በአጽንዖት ተገልጾአል (ከ37፥26፤ 41፥4:26 ጋር ያነጻጽሩ)።

40፥22 *ክበብ፤* ኢዮ22፥14፤ ምሳ8፥27 ይመ። *ሰማያትን በዙፋን ላይ ይቀመጣል፤* ከ66፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ 37፥16 እና ማብ ይመ። *እንደ ድባብ ... እንደ ...ድንኳንም፤* 42፥5፤ 44፥24፤ 51፥13፤ መዝ19፥4፤ 104፥2 ይመ።

40፥23 *አለቆችን ... ገዦች እንዳልነበሩ ያደርጋቸዋል፤* ቍ17፤ 2፥22 እና ማብ ይመ፤ ከኤር25፥17-26፤ ዳን2፥21 ጋር ያነጻጽሩ።

40፥24 *ዐውሎ ነፋስም እንደ ገለባ፤* 17፥13 እና ማብ ይመ፤ 41፥15-16 ይመ።

[25]ቅዱሱ፣ "ከማን ጋር ታወዳድሩኛላችሁ?
የሚስተካከለኝስ ማን አለ?" ይላል።
[26]ዐይናችሁን አንሡ፤ ወደ ሰማይ ተመልከቱ፤
እነዚህን ሁሉ የፈጠረ ማን ነው?
የከዋክብትን ሰራዊት አንድ በአንድ
የሚያወጣቸው፣
በየስማቸው የሚጠራቸው እርሱ ነው።
ከኀይሉ ታላቅነትና ከችሎታው ብርታት
የተነሣ፣
አንዳቸውም አይጠፉም።

[27]ያዕቆብ ሆይ፤ ለምን እንዲህ ትላለህ?
እስራኤል ሆይ፤ ለምን እንዲህ ትናገራለህ?
"መንገዴ *ከእግዚአብሔር* ተሰውራለች፤
ፍርዴም በአምላኬ ቸል ተብላለች"
ለምን ትላለህ?
[28]አታውቅምን?
አልሰማህምን?
*እግዚአብሔር* የዘላለም ስምላክ፣
የምድር ዳርቻ ፈጣሪ ነው።
አይደክምም፤ አይታክትም፤
ማስተዋሉም በማንም አይመረመርም።
[29]ለደከመው ብርታት ይሰጣል፤
ለዛለው ጒልበት ይጨምራል።
[30]ወጣቶች እንኳ ይደክማሉ፤ ይታክታሉም፤
ጐበዛዝትም ተሰናክለው ይወድቃሉ።
[31]*እግዚአብሔርን* ተስፋ የሚያደርጉ ግን፣
ኀይላቸውን ያድሳሉ፤
እንደ ንስር በክንፍ ይወጣሉ፤
ይሮጣሉ፤ አይታክቱም፤
ይሄዳሉ፤ አይደክሙም።

ኢዮ22፥14፤26፥7፤
40፥25 1ሳሙ2፥2፤
1ዜና16፥25፤ኢሳ1፥4፤
37፥23
40፥26 ቍ28፤
2ነገ17፥16፤ነህ9፥6፤
ኢዮ9፥4፤38፥32፤
መዝ89፥11-13፤
ኢሳ34፥16፤42፥5፤
45፥24፤51፥6፤66፥2፤
ኤፌ1፥19
40፥27 ኢዮ6፥29፤
27፥2፤ሉቃ18፥7-8
40፥28 ቍ21፡26፤
ዘዳ33፥27፤መዝ90፥2፤
147፥5፤ኢሳ37፥16፤
44፥12፤ሮሜ11፥33
40፥29 ዘፍ18፥14፤
መዝ68፥35፤119፥28፤
ኢሳ50፥4፤57፥19፤
ኤር31፥25
40፥30 መዝ20፥8፤
ኢሳ5፥27፤9፥17፤
ኤር6፥11፤9፥21፤
40፥31 ዘፀ19፥4፤
1ሳሙ2፥4፤2ነገ6፥33፤
መዝ37፥9፤40፥1፤
ኢሳ30፥18፤ሉቃ18፥1፤
2ቆሮ4፥1፡16፤
ዕብ12፥1-3
41፥1 1ሳሙ2፥4፤
መዝ37፥7፤ኢሳ1፥18፤
11፥11፤34፥1፤48፥16፤
50፥8፤57፥3፤ዕን2፥20፤
ሶፎ1፥7፤ዘካ2፥13
41፥2 ቍ25፤
2ሳሙ22፥43፤
ዕዝ1፥2፤መዝ1፥4፤
ኢሳ13፥4፡17፡18፤
40፥24፤44፥28፤45፥1፡
8፡13፤48፥14፤
ኤር25፥9፤50፥3፤
51፥11
41፥3 ዳን8፥4

## የእስራኤል ረዳት

**41** "ደሴቶች ሆይ፤ በፊቴ ዝም በሉ፤
አሕዛብ ኀይላቸውን ያድሱ፤
ቀርበው ይናገሩ፤
በፍርድም ፊት እንገናኝ።

[2]"ከምሥራቅ አንዱን ያነሣው፣
በጽድቅም ወደ አገልግሎቱ የጠራው
ማን ነው?[*]
አሕዛብን አሳልፎ ሰጠው፤
ነገሥታትን በፊቱ አስገዛለት
በሰይፉም እንደ ትቢያ አቦነናቸው፤
በቀስቱም በነፋስ እንደ ተበተነ ገለባ
አደረጋቸው።
[3]አሳደዳቸው ያለ ችግር ዐልፎ ሄደ፤
እግሩም ቀድሞ ባልረገጠው መንገድ ተጓዘ።
[4]ይህን የሠራና ያደረገ፣
ትውልድን ከጥንት የጠራ ማን ነው?
እኔ *እግዚአብሔር* ከፊተኛው፣
ከኋለኛውም ጋር፤ እኔው ነኝ።"
[5]ደሴቶች አይተው ፈሩ፤
የምድር ዳርቾች ደነገጡ፤
ቀረቡ፤ ወደ ፊትም መጡ።
[6]እያንዳንዱ ይረዳዳል፤
ወንድሙንም፣ "አይዞህ" ይለዋል።
[7]ባለጅ የወርቅ አንጥረኛውን ያበረታታዋል፤
በመዶሻ የሚያሳሳውም፣
በመስፍ ላይ የሚቀጠቅጠውን ያነቃቃዋል፤

ዘፍ1፥1፤ዘዳ32፥39፤ኢሳ43፥7፤44፥6፤46፥10፤ 48፥12፤ራእ1፥8፡17
41፥5 ዘዳ30፥4፤ኢሳ11፥11፡12፤ሕዝ26፥17-18 41፥6 ኢሱ1፥6
41፥7 1ሳሙ5፥3፤ኢሳ40፥19፤44፥13፤46፥7፤ኤር10፥3-5

[*]2 *ወይም በእያንዳንዱ እርምጃ ድል የሚያጋጥመው*

*40፥25፤* ቍ18 ይመ። አንዳንድ ተጠራጣሪ እስራኤላውያን አምላካቸውን እግዚአብሔርን ከማረኳቸው ባቢሎናውያን አማልክት ጋር አወዳድረው፣ እንደ ተሸናፊ አድርገው ሳይቈጥሩት አልቀረም። *ቅዱሱ፤* 1፥4 እና ማብ ይመ።

40፥26 *ፈጠረ፤* ቍ21-22 እና ማብ ይመ። *የሚያወጣቸው፤* ይህ አባባል በዕብራይስጥ በኢዮ38፥32 የተጠቀሱትን ከዋክብት በሥርዐት የሚያስወጣና የሚያስገባ የሚለውን ሐሳብ የያዘ ነው። *የከዋክብትን ሰራዊት፤* በሕዝቡ ይመለኩ ነበር (47፥13፤ ኤር19፥13 ይመ)። *በየስማቸው፤* መዝ147፥4 ይመ። *አንዳቸውም አይጠፉም፤* 34፥16 እና ማብ ይመ።

*40፥27-31፤* በብዙዎቹ የውዳሴ መዝሙሮች ላይ እንደሚታየው፣ ኢሳይያስ የእግዚአብሔርን ክብርና ግርማ አብዝቶ ከገለጸ በኋላ (ቍ12-26) ደግሞ አሁን መልካምነቱን በአጽንዖት ይናገራል። የተጨነቀው ሕዝቡ እንዲህ ያለው አምላክ ሥራውን እንዲሠራ በእምነት ቢጠብቀው ነጻ ሊያወጣውና ሊመልሰው ችሎታው አለው። ሕዝቡ በእርሱ መታመንና ከእርሱም ዘንድ ኀይል ማግኘት አለባቸው።

40፥27 *መንገዴ፤* ሁኔታን የሚያመለክት ነው። *ተሰውራለች ... ፍርዴን ቸላ ብሎአል፤* ከ49፥14፤ 54፥8 ጋር ያነጻጽሩ።

40፥28 *የዘላለም አምላክ፤* 9፥6 ይመ። *ፈጣሪ፤* ቍ21-22 እና ማብ ይመ። *የምድር ዳርቻ፤* 11፥12 እና ማብ ይመ። ከ5፥26፤ 41፥9፤ 43፥6 ጋር ያነጻጽሩ። *አይደክምም፤* ከ44፥12 ጋር ያስተያዩ።

40፥30 *ይደክማሉ ... ተሰናክለው ይወድቃሉ፤* የ5፥27 ማብ ይመ።

40፥31 *ተስፋ የሚያደርጉ፤* መታመን ወይም መጠበቅ ማለት ነው (5፥2፤ 49፥23 ይመ)። *ያድሳሉ፤* ይለውጣሉ ማለት ነው። ድካማቸው በእግዚአብሔር ኀይል ይለወጣል (ቍ29)። የዚህ ቃል ግሥ በዕብራይስጥ ቋንቋ ልብስ መቀየር እንደ ማለት ነው (ዘፍ35፥2፤ መሳ14፥12)፤ ስለዚህ ውበትንና ጥንካሬን ያመለክታል (ኢሳ52፥1)። ሐዋርያው ጳውሎስ አማኞች ክርስቶስን መልበስ ይገባቸዋል በማለት ያስተምራል (ሮሜ13፥14 ይመ፤ ከኤፌ4፥24፤ ቈላ3፥10 ጋር ያነጻጽሩ)። *ንስር፤* በብርታቱና (መዝ103፥5) በፍጥነቱ (ኤር4፥13፤ 48፥40) ይታወቃል።

41፥1፡5 *ደሴቶች፤* ወይም የባሕር ጠረፎች ማለት ነው (11፥11 እና ማብ ይመ)።

41፥1 *ኀይላቸውን ያድሱ፤* 40፥31 ይመ። አሕዛብና አማልክታቸው የእስራኤል አምላክ ያለውን ኀይል እነርሱም እንዲያሳዩ ሲጠየቁ ነው (ቍ21-24 ይመ)።

41፥2 *ከምሥራቅ አንዱን፤* ባቢሎንን በ539 ዓ.ቅ.ክ ላይ (13፥17 እና ማብ ይመ) ያሸነፈውንና አይሁድ ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመለሱ ትእዛዝ የሰጠውን (ዕዝ1፥1-4፤ 6፥3-5) የፋርስ ንጉሥ ታላቁን ቂሮስን ነው (ከ559-530 ዓ.ቅ.ክ)። ቂሮስ በቍ 25፤ 44፥28-45፥5፡13፤ 46፥11 ተጠቅሶአል። *በጽድቅም ... የጠራው፤* በ42፥6 ላይ እንደ ተጠቀሰው የጌታ አገልጋይ ቂሮስም የእግዚአብሔርን ዐላማ የሚፈጽምበትን የጽድቅ ሥራ እንዲሠራ ተመርጦአል። *ነገሥታትን ... አስገዛለት፤* በትንሹ እስያ የሊድያ ንጉሥ እንደ ነበረው እንደ ክሮሰስ ዐይነቶቹን ለማለት ነው። *እንደ ተበተነ ገለባ፤* 17፥13 እና ማብ ይመ። *በቀስቱም፤* የፋርስ ሰዎች በቀስተኛነት እጅግ የታወቁ ነበሩ።

41፥4 *ከጥንት፤* 40፥21 እና ማብ ይመ። *ከፊተኛው፣ ከኋለኛውም፤* እግዚአብሔር ከፊተኞቹ ትውልዶች ጋር አብሮ እንደ ነበረ ሁሉ፣ ከኋለኞችም ጋር እንዲሁ አብሮ ይሆናል። እግዚአብሔር በታሪክና በመንግሥታት ሁሉ ላይ የዘላለም ጌታ ነው (ዕብ13፥8፤ ራእ1፥8፡17፤ 2፥8፤ 21፥6፤ 22፥13 ይመ)።

*41፥5-7፤* ቂሮስ በ546 ዓ.ቅ.ክ ላይ ዋና ተቃዋሚው የሆነውን የሊድያን ንጉሥ ክሮሰስን አሸንፎ በድል አድራጊነት ወደ እስያ ምዕራብ ጠረፍ ግዛት ገባ። የጣላቶቹ ከንቱ ትብብር በአሽሙርና በፌዝ አገላለጽ ቀርቦአል (ከ40፥19-20 ጋር ያነጻጽሩ)።

41፥5 *የምድር ዳርቾች፤* 11፥12 እና ማብ ይመ።

41፥6 *አይዞህ፤* 35፥4 እና ማብ ይመ።

41፥7 *መዶሻ፤* ከ44፥12 ጋር ያነጻጽሩ። *እንዳይወድቅም፤* 40፥18-20 እና ማብ ይመ።

ስለ ብየዳም ሥራው፣ "መልካም ነው" ይለዋል፤
የጣዖቱ ምስል እንዳይወድቅም በምስማር
ያጣብቀዋል::

[8]"አንተ ግን፣ ባሪያዬ እስራኤል፣
የመረጥሁ ያዕቆብ፣
የወዳጄ የአብርሃም ዘር ሆይ፤
[9]ከምድር ዳርቻ ያመጣሁህ፣
ከአጥናፍም የጠራሁህ፣
'አንተ ባሪያዬ ነህ' ያልሁህ፤
መረጥሁህ እንጂ፤ አልጣልሁህም::
[10]እኔ ከአንተ ጋር ነኝና አትፍራ፤
አምላክህ ነኝና አትደንግጥ::
አበረታሃለሁ፤ እረዳሃለሁ፤
በጽድቄም ቀኝ እጄ ደግፌ እይዝሃለሁ::
[11]"እነሆ፤ የተቈጡህ ሁሉ፣
እጅግ ያፍራሉ፤ ይዋረዳሉም፤
የሚቋቋሙህ፣
እንዳልነበሩ ይሆናሉ፤ ይጠፋሉም::
[12]ጠላቶችህን ብትፈልጋቸው እንኳ፣
አታገኛቸውም፤
የሚዋጉህም፣
እንዳልነበሩ ይሆናሉ::
[13]እኔ *እግዚአብሔር* አምላክህ
'አትፍራ፤
እረዳሃለሁ'
ብዬ ቀኝ እጅህን እይዛለሁና::
[14]አንት ትል ያዕቆብ፣
ታናሽ እስራኤል ሆይ፤
'አትፍራ እኔ እረዳሃለሁ' "
ይላል እግዚአብሔር፤
የሚቤዥህ
የእስራኤል ቅዱስ ነው::

[15]"እነሆ፣ አዲስ
የተሳለና ብዙ ጥርስ ያለው ማሄጃ አደርግሃለሁ፤
ተራሮችን ታሄዳለህ፤ ታደቃቸዋለህ፤
ኰረብቶችንም ገለባ ታደርጋቸዋለህ::
[16]ታበጥራቸዋለህ፤ ነፋስ ጠርጎ ይወስዳቸዋል፤
ዐውሎ ነፋስም ይበትናቸዋል::
አንተ ግን *በእግዚአብሔር* ደስ ይልሃል፤
በእስራኤል ቅዱስ ሞገስ ታገኛለህ::

[17]"ድኾችና ችግረኞች ውሃ ይፈልጋሉ፤
ዳሩ ግን ምንም አያገኙም፤
ጕሮሮአቸው በውሃ ጥም ደርቆአል::
ነገር ግን እኔ *እግዚአብሔር* እመልስላቸዋለሁ፤
እኔ የእስራኤል አምላክ አልተዋቸውም::
[18]በተራቈቱ ኰረብቶች ላይ ወንዞችን፣
በሸለቆዎች ውስጥ ምንጮች አፈልቃለሁ::
ምድረ በዳውን የውሃ ኵሬ፣
የተጠማውን ምድር የውሃ ምንጭ አደርጋለሁ::
[19]በምድረ በዳ፣
ዝግባን፣ ግራርን፣ ባርሰነትንና ወይራን
አበቅላለሁ፤
በበረሃ፣
ጥድን፣ አስታንና ሸውሸዌን በአንድነት
እተክላለሁ::
[20]ስለዚህ ሰዎች ያያሉ፤ ያውቃሉ፤
*የእግዚአብሔር* እጅ ይህን እንዳደረገ፣
የእስራኤል ቅዱስ እንደ ፈጠረው፣
በአንድነት ይገነዘባሉ፤ ያስተውላሉም::

41፥4 ቍ9:26፤
41፥8 2ዜና20፥7፤ መዝ136፥22፤ ኢሳ14፥1፤27፥11፤ 29፥22፤51፥2፤63፥16፤ ያዕ2፥23
41፥9 ቍ4፤ ዘዳ7፥6፤ኢሳ11፥12፤ 20፥3፤37፥16
41፥10 ቍ13-14፤ ዘፍ15፥1፤ዘፀ3፥20፤ ዘዳ3፥22፤ኢሱ1፥9፤ ኢዮ40፥14፤ መዝ18፥35፤68፥35፤ 119፥28:117፤ ኢሳ43፥2:5፤44፥2፤ 49፥8፤50፥7:9፤ ኤር30፥10፤46፥27-28፤ ሮሜ8፥31
41፥11 ዘፀ23፥22፤ ኢሳ17፥12፤29፥8:22፤ 45፥24፤54፥17፤ ኤር2፥3
41፥12 ኢዮ7፥8፤ መዝ37፥35-36፤ ኢሳ17፥14፤29፥20፤ 34፥12
41፥13 ቍ10፤ መዝ73፥23፤ኢሳ42፥6፤ 45፥1፤51፥18
41፥14 ቍ10:16: 20፤ዘፍ15፥1፤ ዘፀ15፥13፤ኢዮ4፥19፤ 19፥25፤መዝ22፥6፤ ኢሳ1፥4:27
41፥15 ቍ2፤ ዘፀ19፥18፤ኢዮ41፥30፤ መዝ107፥33፤ ኢሳ10፥5፤21፥10፤ ኤር9፥10፤ሕዝ33፥28
41፥16 ቍ14፤ ኢሳ25፥9፤40፥24፤ 45፥25፤ 60፥19፤ ኤር15፥7፤51፥2፤ ዳን2፥35፤ማር1፥24
መዝ27፥9፤ኢሳ30፥19፤ 35፥7፤43፥20 41፥18 2ነገ3፥17፤ኢዮ38፥26፤ ኢሳ30፥25፤35፥7፤43፥19 41፥19 ዘፀ25፥5:10፤ኢሳ35፥1፤37፥24፤ 44፥14፤51፥3፤60፥13 41፥20 ቍ14፤ዘፀ6፥7፤ዕዝ7፥6፤ 8፥31፤ ኢሳ4፥5፤ 29፥24፤43፥3:14፤50፥2፤51፥1:9፤59፥1፤66፥14፤ኤር32፥17

41፥8-9 *ባሪያዬ፤* አንዳንድ ጊዜ የእስራኤልን ሕዝብ፣ በሌላ ጊዜ ደግሞ አንድን ግለሰብ ለማመልከት ከምዕራፍ 41-53 ባሉት ክፍሎች ላይ የሚጠቀስ ዋና ቃል ነው:: በእነዚህ ምንባቦች ቃሉ በእግዚአብሔር መንግሥት አስተዳደር ውስጥ ልዩ ሥልጣን የተሰጠውን ሰው ያመለክታል ለምሳሌ፣ "ባሪያዎቹ ነቢያት" (2ነገ17፥13፤ ኤር7፥25)፤ የ42፥1 ማብ ይመ:: 20፥3፤ 22፥20፤ 42፥1:19፤ 43፥10፤ 44፥1-2:21፤ 45፥4፤ 49፥3:5-7፤ 50፥10፤ 52፥13፤ 53፥11 ይመ::

41፥8 *ግን፤* ከቍ5-7 ላይ የተጠቀሱትን አሕዛብ የሚያነጻጽር ቃል ነው፤ እስራኤል መፍራት አይገባትም (ቍ10):: *የወዳጄ፤* ዘፍ18፤ 2ዜና20፥7፤ ያዕ2፥23 ይመ:: አንዳንዶች፣ "ወዳጄ" የሚለውና "የመረጥሁህ" የሚለው የእስራኤልን ዘር በሙሉ የሚያመለክት ነው ይላሉ::

41፥9 *ከምድር ዳርቻ፤* ቍ5 ይመ፤ ምናልባትም ግብፅንና መስጴጦምያን የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (ዘፍ11፥31፤ 12፥1፤ 15፥7፤ መዝ114፥1-2፤ ኤር31፥32 ይመ)::

41፥10 *አትፍራ ... አትደንግጥ፤* ቍ13-14፤ 43፥1:5 ይመ:: 35፥4 እና ማብ ይመ:: *አበረታሃለሁ፣ እረዳሃለሁ፤* ለእግዚአብሔር ሥራ እንደ ተጠራ ሰው ማለት ነው (ቍ9:15-16 ይመ):: ቍ14፤ 40፥29፤ 44፥2፤ 49፥8 ይመ:: *ቀኝ እጄ፤* የኀይልና የማዳን እጅ ነው (ዘፀ15፥6:12፤ መዝ20፥6፤ 48፥10፤ 89፥13፤ 98፥1 ይመ)::

41፥11 *ያፍራሉ፤ ይዋረዳሉም፤* ከ45፥17፤ 50፥7፤ 54፥4 ጋር ያነጻጽሩ:: *እንዳልነበሩ ይሆናሉ፤* ቍ15-16 እና ማብ ይመ::

*41፥13 ቀኝ እጅህን እይዛለሁና፤* እንዲበረታቱና እንዳይሰናከሉ ለማድረግ ነው:: *አትፍራ፤* ቍ10 እና ማብ ይመ::

41፥14 *ትል፤* በምርኮው ወቅት የነበረውን ሁኔታ ያሳያል (ከኢዮ25፥6 ጋር ያነጻጽሩ):: *የሚቤዥህም፤* ከባቢሎን ምርኮ ነጻ የሚያወጣ ማለት ነው:; የዚህ ቃል የዕብራይስጥ ትርጕም ቤተ ሰብን ከአደጋ የሚጠብቅ ግዴታ ያለበትን ሰው ሲያመለክት፣ እግዚአብሔርም የእስራኤልን ቤት የሚጠብቅ መሆኑን በምሳሌ ያሳያል:: እግዚአብሔር ለእስራኤል እንደ አባት (63፥16፤ 64፥8) እና እንደ ባል (54፥5) በመሆን ተዛምዶአል:: እንደ ቤዛ ወይም እንደ ቤተ ሰብ ጠባቂና ተንከባካቢ የእስራኤልን ንብረት ይዋጃል (ወደ አገራቸው ሰብስቦ ይመልሳቸዋልና 54፥1-8)፤ ለነጻነታቸው ዋስትና ይሰጣቸዋል (35፥9፤ 43፥1-4፤ 48፥20፤ 52፥11-12)፤ ያስጨነቋቸውን ይበቀልላቸዋል (47፥3፤ 49፥25-26፤ 64፥4)፤ ለወደፊቱም ይዞታቸውን ያረጋግጥላቸዋል (61፥8-9):: የሩት 2፥20 ማብ ይመ:: *የእስራኤል ቅዱስ፤* ቍ16:20 ይመ:: 1፥4 እና ማብ ይመ:: በ43፥14፤ 47፥4፤ 48፥17፤ 49፥7፤ 54፥5 "የሚቤዣችሁ" ተብሎ ተጠቅሶአል::

41፥15 *ማሄጃ፤* ከ28፥27፤ ሚክ4፥13፤ ዕን3፥12 ጋር ያነጻጽሩ:: *ተራሮችን ... ኰረብቶችንም፤* ምናልባት አሕዛብን ሊያመለክት ይችላል፤ 2፥14 ይመ:: *ገለባ ታደርጋቸዋለህ፤* ቍ2፤ 17፥13 እና ማብ፤ 29፥5-6 ይመ::

41፥16 *ታበጥራቸዋለህ፤* ፍርድን የሚመለከት ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው፤ በኤር51፥2 ላይም ተጠቅሶአል:: *ደስ ይልሃል፤* ከ25፥9፤35፥10፤51፥11 ጋር ያነጻጽሩ::

41፥17 *ድኾችና ችግረኞች፤* በምርኮ ያሉትን ወይም ወደ አገራቸው ለመመለስ በመንገድ ላይ ያሉትን እስራኤላውያን የሚያመለክት ነው (ከቍ14፤ 32፥7 ጋር ያነጻጽሩ):: *እመልስላቸዋለሁ፤* 30፥19 እና ማብ ይመ::

41፥18 *በተራቈቱ ኰረብቶች ላይ ወንዞችን፤* 30፥25 እና ማብ ይመ:: *ምድረ በዳውን የውሃ ኵሬ ...የውሃ ምንጭ፤* 32፥2፤ 35፥6-7 እና ማብ ይመ::

*41፥19፤* እነዚህ ዛፎች ለምድረ በዳው ውበትን ያላብሱታል (ከ35፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ):: ብዙዎቹ በ60፥13 ላይ የእግዚአብሔርን ማደሪያ ለማስጌጥ ጥቅም ላይ እንደ ዋሉ ተጠቅሶአል:: የግራር ዕንጨት በማደሪያው ድንኳን ውስጥ ለአገልግሎት ውሏል (ዘፀ 25፥5:10:13) የጥድ ዛፍና ባርሰነት በ55፥13 የተጠቀሰውን እሾኽና ኵርንችት የሚተኩ ይሆናሉ::

41፥20 *እንደ ፈጠረው፤* እነዚህ የተጠቀሱት ፍሬያማ ሁኔታዎች እግዚአብሔር ለሕዝቡ ሲል አዲስ ከፈጠረው አዲስ

[21]“ሙግታችሁን ይዛችሁ ቅረቡ” ይላል
እግዚአብሔር፤
“ማስረጃችሁን አምጡ” ይላል የያዕቆብ
ንጉሥ::
[22]“የሚሆነውን እንዲነግሩን፣
ጣዖቶቻችሁን አምጡ፤
እንድንገነዘብ፣
ፍጻሜአቸውን እንድናውቅ፣
የቀደሙት ነገሮች ምን እንደ ነበሩ ንገሩን፤
ስለሚመጡትም ነገሮች ግለጹልን::
[23]እናንተ አማልክት መሆናችሁን እናውቅ
ዘንድ፣
ወደ ፊት ስለሚሆነው ንገሩን፤
እንድንደነግጥ፣ በፍርሀት እንድንዋጥ፣
መልካምም ሆነ ክፉ፣ አንድ ነገር አድርጉ::
[24]እነሆ፤ እናንተ ከምንም የማትቈጠሩ ናችሁ፤
ሥራችሁ ፈጽሞ ዋጋ ቢስ ነው፤
የመረጣችሁም አስጸያፊ ነው::
[25]“አንዱን ከሰሜን አስነሣሁት፤ እርሱም
ይመጣል፤
ከፀሓይ መውጫ የሚመጣው፣ ስሜን
የሚጠራ ነው፤
ሸክላ ሠሪ ዐፈር እንደሚረግጥ፣
አለቆችን እንዲሁ እንደ ጭቃ ይረግጣል::
[26]እኛ እናውቅ ዘንድ ይህን ከመጀመሪያው
የተናገረ፣
‘እርሱ ትክክል ነው’ እንልም ዘንድ ቀድሞ
የተናገረ ማነው?
ማንም አልተናገረም፤
ቀድም ብሎ የተናገረ የለም፤
ቃላችሁንም የሰማ የለም::
[27]በመጀመሪያ፣ ‘እነሆ፤ ተመልከቷቸው!’
ብዬ ለጽዮን የተናገርሁ እኔ ነበርሁ፤
ለኢየሩሳሌምም
የምሥራች ነጋሪን ሰጥቻለሁ::
[28]ተመለከትሁ ማንም አልነበረም፤
ከመካከላቸው አማካሪ የለም፤
ስጠይቅም መልስ የሚሰጥ የለም::
[29]እነሆ፤ ሁሉም ከንቱ ናቸው፤
ሥራቸውም መና ነው፤
ምስሎቻቸውም ባዶ ነፋስ ናቸው::

## የእግዚአብሔር አገልጋይ

# 42

“ደግፌ የያዝሁት አገልጋዬ፣
በእርሱም ደስ የሚለኝ ምርጤ
ይህ ነው፤
መንፈሴን በእርሱ ላይ አደርጋለሁ፤
ለአሕዛብም ፍትሕን ያመጣል::
[2]አይጮኽም፣ ቃሉን ከፍ አያደርግም፤
ድምፁን በመንገድ ላይ በኀይል አያሰማም::
[3]የተቀጠቀጠ ሸምበቆ አይሰብርም፤
የሚጤስም የጧፍ ክር አያጠፋም፤
ፍትሕን በታማኝነት ያመጣል::
[4]ፍትሕን በምድር እስኪያመጣ ድረስ፣
አይደክምም፤ ተስፋም አይቈርጥም፤
ደሴቶች በሕጉ ይታመናሉ::”
[5]ሰማያትን የፈጠረ፣ የዘረጋቸውም፣
ምድርንና በውስጧ ያሉትን ሁሉ ያበጀ፣
ለሕዝቧ እስትንፋስን፣
ለሚኖሩባትም ሕይወትን የሚሰጥ፣

41፥21 ቍ1፤ ኢሳ43፥15፤44፥6
41፥22 ቍ26፤ ኢሳ42፥9፤43፥9:18፡ 19:26፤44፥7፤45፥21፤ 46፥9:10፤48፥3:6:14፤ 65፥17፤ዮሐ13፥19
41፥23 2ነገ19፥26፤ ኢሳ45፥3፤ኤር10፥5
41፥24 1ሳሙ12፥21፤ መዝ109፥7፤ኢሳ1፥13፤ 37፥19፤48፥8፤ ኤር8፥19፤10፥5:8:15፤ 1ቆሮ8፥4
41፥25 ቍ2፤ 2ሳሙ22፥43፤ዕዝ1፥2፤ ኢሳ5፥5፤ኤር50፥9:41፤ 51፥48፤ናሆ3፥14
41፥26 ቍ4:22፤ 1ነገ18፥26፤ኢሳ52፥6፤ ዕን2፥18-19
41፥27 ኢሳ40፥9፤ 48፥3:16
41፥28 1ነገ18፥26፤ መዝ22፥11፤ ኢሳ40፥13-14፤ 50፥2፤59፥16፤63፥5፤ 64፥7፤65፥12፤66፥4፤ ኤር25፥4፤ሕዝ22፥30
41፥29 1ሳሙ12፥21፤ ኢሳ37፥19፤ኤር5፥13
42፥1 ዘፍ49፥10፤ ኢሳ9፥7፤11፥2፤14፥1፤ 20፥3፤44፥3፤ ማቴ3፥16-17፤ 20፥28፤ሉቃ9፥35፤ 23፥35፤ዮሐ3፥34፤ 1ጴጥ2፥4:6 ዘፍ49፥10፤ዘፀ34፥29፤ኢሳ2፥4፤11፥11፤51፥4፤ማቴ12፥18-21
42፥2 ምሳ8፥1-2
42፥3 ኢዮ13፥25፤ 30፥24፤መዝ72፥2፤ 96፥13፤ኢሳ36፥6
42፥4 ቍ21፤
42፥5 ዘፍ1፥1:6፤2፥7፤መዝ24፥2፤102፥25፤ኢሳ48፥13፤ሐሥ17፥24:25

ፍጥረት ከፊሉ ናቸው (48፥7፤ 57፥19፤ 65፥17-18 ይመ)::

*41፥21-22፤* እግዚአብሔር አሕዛብን ከነጣዖቶቻቸው ለፍርድ እንደሚያቀርባቸው ያመለክታል::

41፥22 የቀደሙት ነገሮች፤ ቀደም ብለው የተነገሩትንና የተፈጸሙትን ለማለት ነው(42፥9፤ 43፥9:18፤ 46፥9፤ 48፥3 ይመ)::

41፥23 *መልካምም ሆነ ክፉ፣ አንድ ነገር አድርጉ፤* የ40፥18-20 ማብ ይመ::

41፥24 *ከምንም የማትቈጠሩ ናችሁ ... ዋጋ ቢስ ነው፤* እንደሚያመልኳቸው እንደ አሕዛብ እነርሱም እንዲሁ ናቸው፤ 40፥17፤ 44፥9፤ ሆሴ9፥10 ይመ:: *አስጸያፊ፤* ጣዖት አምላኪዎችን እንደሚያገቡ ሰዎች ማለት ነው (ሚል2፥11 ይመ)::

41፥25 *አስነሣሁት፤* ቍ2 እና ማብ ይመ:: *ከሰሜን፤* ቂሮስ የተነሣው ከምሥራቅ ነው (ቍ2)፤ ነገር ግን በቀደመው የግዛት ዘመኑ ከባቢሎን በስተ ሰሜን ያሉትን አገሮች ገዝቶ ነበር:: እንደ መካከለኛው ምሥራቅ ጸሓፊዎች አመለካከት ወረራዎች በአብዛኛው የተነሡት ከሰሜን ነበር (14፥31፤ ኤር1፥14፤ 6፥1:22፤ 10፥22፤ 46፥20፤ 50፥3:9:41፤ 51፥48 ይመ):: *ስሜን የሚጠራ፤* ቂሮስ ዐዋጁን ሲያውጅ የእግዚአብሔርን ስም ጠርቶ ነበር (ዕዝ1፥2)፤ ይሁን እንጂ እግዚአብሔርን አያውቅም (45፥4-5 ይመ):: *ሸክላ ... እንደ ጭቃ ይረግጣል፤* በ10፥6 ስለ አሦር ከተነገረው ጋር ይመሳሰላል፤ ከናሆ3፥14፤ ሚክ7፥10 ጋር ያነጻጽሩ::

41፥26 *ከመጀመሪያው፤* እነዚህ ሁሉ ሁኔታዎች ከመጀመ ራቸው በፊት ለማለት ነው (ከቍ4 ጋር ያነጻጽሩ):: *ቃላችሁንም፤* ጣዖቶችንና ወይም የሚያመልኳቸውን ማለት ነው::

41፥27 *እነሆ፤ ተመልከቷቸው፤* ከባቢሎን ነጻ ስለ መውጣት የተነገረ ቃል ነው:: *የምሥራች ነጋሪን፤* ኢሳይያስን ነው፤ 40፥9፤ 52፥7 እና ማብ ይመ::

41፥28 *መልስ የሚሰጥ የለም፤* 46፥7 ይመ::

41፥29 *ሥራቸውም መና ነው፤* ቍ24 ይመ::

*42፥1-4፤* በከፊል በማቴ12፥18-21 ክርስቶስን በማስመልከት ተጠቅሶአል:: አገልጋይ የተባለው መሲሑ መሆኑን የሚያመለክቱ፣ “አራት የአገልጋይ መዝሙሮች” አሉ:: እነርሱም 42፥1-4 (ወይም 42፥1-7 ወይም 42፥1-9)፤ 49፥1-6 (ወይም 49፥1-7 ወይም 49፥1-13)፤ 50፥4-9 (ወይም50፥4-11)፤ 52፥13-53፥12 ናቸው:: አገልጋይ በ49፥3 ላይ እንደ ተጠቀሰው፣ “እስራኤል” ነው:: የእስ ራኤል መንግሥት የካህናት መንግሥት ነው (ዘፀ19፥6)፤ ይሁን እንጂ መሲሑ የዓለምን ሁሉ ኀጢአት የሚያስወግድ ሊቀ ካህናት ነው (53፥4-12):: በምዕራፍ 41 ላይ ቂሮስ እስራኤልን ከባቢሎን ነጻ እንደሚያወጣ ተጠቅሶአል፤ አገልጋዩ ግን ዓለምን ከኀጢአት ባርነት ነጻ የሚያወጣው ነው (ቍ7 ይመ)::

42፥1 *አገልጋዬ፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ፤ ዘካ3፥8 ይመ:: ጥንት በመካከለኛው ምሥራቅ መንግሥታዊ አገላለጽ፣ “አገልጋይ” ሲባል፣ “ታማኝ መልእክተኛ” ወይም “አስተማማኝ ወኪል” በሚል ሊተረጐም ይችላል:: *ደስ የሚለኝ፤* ከሉቃ3፥22 ጋር ያነጻጽሩ:: *ምርጤ፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ:: *መንፈሴን በእርሱ ላይ፤* በ11፥2 ላይ እንደ ተጠቀሰው፣ “ቀኍጥቋጥ” ማለት ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)፤ ከ61፥1 ጋር ያነጻጽሩ:: *ፍትሕን፤* ጽድቅ የሰፈነበት የዓለም ሥርዐት ነው (ቍ4 ይመ)፤ 9፥7 እና ማብ ይመ፤ 11፥4 እና ማብ ይመ::

42፥2 *አይጮኽም፤ ቃሉን ከፍ አያደርግም፤* ሰላምን ያመጣል ማለት ነው (9፥6 ይመ)::

42፥3 *የተቀጠቀጠ ሸምበቆ፤* ደካማ የሆነ ማለት ነው (መዝ72፥2:4 ይመ):: አገልጋይ የተሰበሩትን ሰዎች ሕይወት ይጠግናል::

42፥4 *ፍትሕን፤* ፍጹም የሆነ ሕግና ሥርዐት ያሰፍናል ማለት ነው (ቍ1 እና ማብ ይመ):: *አይደክምም፤* ከ40፥28 ጋር ያነጻጽሩ:: *ደሴቶች፤* የ11፥11 ማብ ይመ:: *በሕጉ ይታመናሉ፤* በ2፥2-4 ላይ የተመለከቱት አሕዛብ እንደሚያደርጉት ማለት ነው:: አገልጋይ አዲሱ ሙሴ ይሆናል (ዘዳ18፥15-18፤ ሐሥ3፥21-23 26 ይመ)::

42፥5 *ሰማያትን የፈጠረ፣ የዘረጋ፤* 40፥22 እና ማብ ይመ:: *እስትንፋስን ... ሕይወትን፤* ከ57፥15 ጋር ያነጻጽሩ::

ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
6 “እኔ እግዚአብሔር በጽድቅ ጠርቼሃለሁ፤
እጅህንም እይዛለሁ፤
እጠብቅሃለሁ፤
ለሕዝቡ ቃል ኪዳን፣
ለአሕዛብም ብርሃን አደርግሃለሁ።
7 የዕውሮችን ዐይን ትከፍታለህ፤
ምርኮኞችን ከእስር ቤት፣
በጨለማ የተቀመጡትንም ከወህኒ ታወጣለህ።

8 “እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤ ስሜም ይህ ነው፤
ክብሬን ለሌላ፣
ምስጋናዬንም ለጣዖት አልሰጥም።
9 እነሆ፤ የቀድሞው ነገር ተፈጽሞአል፤
እኔም አዲስ ነገር እናገራለሁ፤
ከመብቀሉም በፊት፣
ለእናንተ አስታውቃለሁ።

### ለእግዚአብሔር የውዳሴ መዝሙር

10 እናንት ወደ ባሕር የምትወርዱ፣ በዚያም ያላችሁ ሁሉ፣
ደሴቶችና በዚያ የምትኖሩ በሙሉ፣
ለእግዚአብሔር አዲስ መዝሙር፣
ከምድር ዳርቻም ምስጋናውን ዘምሩ።
11 ምድረ በዳውና ከተሞቹ ድምፃቸውን ከፍ ያድርጉ፤
ቄዳር ያለችበት መንደር ደስ ይበለው፤
የሴላ ሕዝቦች በደስታ ይዘምሩ፤
ከተራሮችም ራስ ላይ ይጮኹ።
12 ክብር ለእግዚአብሔር ይስጡ፤
ምስጋናውንም በደሴቶች ያውጁ።
13 እግዚአብሔር እንደ ኀያል ሰው ይዘምታል፤
እንደ ተዋጊ በወኔ ይነሣል፤
የቀረርቶ ጩኸት ያሰማል፤
ጠላቶቹንም ድል ያደርጋል።
14 “ለረጅም ጊዜ ዝም አልሁ፤
ጸጥ አልሁ፤ ራሴንም ገታሁ፤
አሁን ግን ምጥ እንደ ያዛት ሴት፣
እጮኻለሁ፤ ቁና ቁና እቃትታለሁ፤
እተነፍሳለሁ።
15 ተራራውንና ኰረብታውን አፈርሳለሁ፤
ዕፀዋቱን ሁሉ አደርቃለሁ፤
ወንዙንም ደሴት አደርጋለሁ፤
ኵሬውን አደርቃለሁ።
16 ዕውሮችን በማያውቁት መንገድ እመራቸዋለሁ፤
ባልተለመደ ጐዳና እወስዳቸዋለሁ።
ጨለማውን በፊታቸው ብርሃን አደርጋለሁ፤
ጐርባጣውን ስፍራ አስተካክላለሁ።
ይህን አደርጋለሁ፤
አልተዋቸውም።
17 በጣዖት የሚታመኑ ግን፣
ምስሎችን፣ ‘አምላኮቻችን ናችሁ’ የሚሉ፣
ወደ ኋላቸው ይመለሳሉ፤ ፈጽመው ይዋረዳሉም።

### ዕውሯና ደንቈሮዋ እስራኤል

18 “እናንት ደንቈሮዎች ስሙ፤
እናንት ዕውሮች እዩ፤ ተመልከቱም።
19 አገልጋዬ እንጂ፣ ሌላ ዕውር ማን አለ?
ከምልከው መልእክተኛዬስ በቀር ማን ደንቈሮ አለ?
ለእኔ ታማኝ እንደ ሆነ ሰው የታወረ፣
እንደ እግዚአብሔርስ አገልጋይ ዕውር ማነው?
20 ብዙ ነገርን አያችሁ፤ ነገር ግን አላስተዋላችሁም፤
ጆሮአችሁ ክፍት ነው፤ ነገር ግን ምንም አትሰሙም።”
21 እግዚአብሔር ስለ ጽድቁ ሲል፣
ሕጉን ታላቅና የተከበረ በማድረግ ደስ አለው።
22 ይህ ሕዝብ ግን የተበዘበዘና የተዘረፈ፣
በጕድጓድ ውስጥ የተጠመደበት፣

42፥4 ቍ21፤
42፥6 ዘፀ31፥2፤ መሳ4፥10፤ ኢሳ9፥2፤ 26፥3:18፤27፥3፤ 41፥9-10:13፤43፥1፤ 45፥1:24፤49፥8፤ 54፥10፤59፥21፤61፥8፤ ኤር23፥6፤31፥31፤ 32፥40፤ዳን9፥7፤ ሚል3፥1፤ሉቃ2፥32፤ 22፥20
42፥7 መዝ66፥11፤ 107፥10:14፤146፥8፤ ኢሳ24፥22፤32፥3፤ 48፥20፤49፥9፤51፥14፤ 52፥2፤ዘካ2፥7፤9፥11፤ ማቴ11፥5፤ሉቃ4፥19፤ ሐሥ26፥18፤ ዕብ2፥14-15፤ 2ጢሞ2፥26
42፥8 ዘፀ3፥15፤ 6፥3:8፥10፤20፥4፤ መዝ81፥10፤ ኢሳ43፥3:11:15፤ 46፥9፤48፥11፤49፥23
42፥9 ኢሳ40፥21፤ 41፥22፤ሕዝ2፥4
42፥10 ዘፀ15፥1፤ ዘዳ30፥4፤1ነገ10፥9፤ 1ዜና16፥32፤ መዝ48፥10፤65፥5፤ 96፥1:11፤ኢሳ11፥11፤ 49፥6፤60፥6
42፥11 ዘፍ25፥13፤ መሳ1፥36፤ኢሳ32፥16፤ 52፥7፤60፥7፤ናሆ1፥15
42፥12 1ዜና16፥24፤ መዝ26፥7፤66፥2፤ ኢሳ11፥11፤24፥15፤ 1ጴጥ2፥9
42፥13 ዘፀ14፥14፤ ኢሉ6፥5፤ኢሳ9፥6፤ 26፥11፤66፥14፤ ኤር25፥30፤ሆሴ11፥10፤ ኢዩ3፥16፤አሞ1፥2፤ 3፥4:8
42፥14 ዘፍ43፥31፤ አስ4፥14፤መዝ50፥21፤ ኤር4፥31፤ ሉቃ18፥7፤2ጴጥ3፥9
42፥15 መዝ107፥33፤ ኢሳ11፥15፤50፥2፤ ሕዝ38፥20፤ናሆ1፥4-6
መዝ18፥28፤ኢሳ26፥7፤29፥24፤32፥3፤40፥11፤57፥18፤58፥8:10:11፤ ኤር31፥8-9፤ ሉቃ1፥78-79፤ 3፥5፤ሐሥ26፥18፤ዕብ13፥5
42፥17 ዘፀ32፥4፤ መዝ97፥7፤ኢሳ1፥29 42፥18 ኢሳ35፥5
42፥19 ኢሳ26፥3፤ 41፥8-9፤43፥8፤44፥26፤ሕዝ12፥2፤ሐጌ1፥13
42፥20 ኢሳ6፥9-10፤ 43፥8፤ኤር5፥21፤6፥10 42፥21 ቍ4፤ ኢሳ43፥25፤2ቆሮ3፥7 42፥22 መሳ6፥4፤2ነገ24፥13፤መዝ66፥11፤ ኢሳ5፥29፤24፥18፥22

42፥6 *በጽድቅ ጠርቼሃለሁ፤* ሁኔታው ቂሮስ ከተጠራበት ጋር ተመሳሳይ ነው (41፥2 እና ማብ ይመ)። *እጅህንም እይዛለሁ፤* 41፥13 እና ማብ ይመ። *ቃል ኪዳን፤* 49፥8 ይመ። እንደ ንጉሥ መሲሑ የዳዊትን ኪዳን ይፈጽማል (9፥7)፤ በሞቱም አዲሱን ኪዳን ይመሠርታል (ኤር31፥31-34፤ ዕብ8፥6-13፤ 9፥15)። *ለሕዝቡ፤* ምናልባት እስራኤላውያንን ሳይሆን አይቀርም (49፥8፤ ሐሥ26፥17-18 ይመ)። *ብርሃን፤* በ49፥6 ከተጠቀሰው “ድነት” ጋር አንድ ዐይነት ነው፤ ከ51፥4 ጋር ያነጻጽሩ።

42፥7 *ዐይን ትከፍታለህ፤* 29፥18፤ 32፥3፤ 35፥5 እና ማብ ይመ። *ከእስር ቤት ...ታወጣለህ፤* ከባቢሎን እስር ቤትና እንዲሁም ከመንፈሳዊና ከግብረ ገብ ባርነት ነጻ መውጣትን ያመለክታል (61፥1 ከሉቃ4፥18 ጋር ያነጻጽሩ)።

42፥8 *ክብሬን፤* 40፥5 እና ማብ ይመ።

42፥9 *የቀድሞው ነገር፤* 41፥22 እና ማብ ይመ። *አዲስ ነገር፤* የእስራኤልን ከምርኮ መመለስ ያመለክታል (43፥19)፤ ከ48፥6 ያነጻጽሩ።

42፥10 *ደሴቶችና፤* ቍ12:11፥11 እና ማብ ይመ። *አዲስ መዝሙር፤* በቍ9 ላይ እንደ ተገለጸው ስለሚከናወነው አዲስ ነገር እግዚአብሔርን ማክበር ነው። *ከምድር ዳርቻም፤* 11፥12 እና ማብ እንዲሁም 41፥5 ይመ።

42፥11 *ምድረ በዳውና፤* 35፥1 እና ማብ ይመ። *ቄዳር፤* የ21፥16 ማብ ይመ። *ሴላ፤* የ16፥1 ማብ ይመ።

42፥12 *ክብር ... ይስጡ፤ ምሥጋናውንም፤* 24፥14-16 ይመ።

42፥13 *ኀያል ሰው፤* እግዚአብሔር በቀይ ባሕር ያደረገውን እዚህ ይደግመዋል (ዘፀ15፥3) 9፥6 እና ማብ ይመ። *በወኔ፤* ከ9፥7፤ 37፥32፤ 59፥17፤ 63፥15 ጋር ያነጻጽሩ። *በቀረርቶ በጩኸት፤* ጠላትን ለማሸበር የሚደረግ (1ሳሙ4፥5-8 ይመ)።

42፥14 *ለረዥም ጊዜ፤* እስራኤላውያን በምርኮ የተጋዙበትና የተዋረዱበት ዘመን ነው። *ራሴንም ገታሁ፤* 63፥15፤ 64፥12 ይመ። የዕብራይስጡ ግሥ፣ ዮሴፍ ወንድሞቹን በጠየቀ ጊዜ ራሱን የተቈጣጠረበትን ሁኔታ ያመለክታል (ዘፍ43፥31፤ 45፥1) 30፥18 እና ማብ ይመ።

42፥15 *አፈርሳለሁ ... አደርቃለሁ፤* የ35፥1-2፤ 41፥18 ተቃራኒ ነው። *ወንዙን ደሴት፤* ምናልባት ጕዞን ለማቅለል ይሆናል፤ 37፥25፤ 44፥27 ይመ።

42፥16 *ዕውሮችን፤* እስራኤልን ለማለት ነው (ቍ19-20)። *ጐርባጣውን ... አስተካክላለሁ፤* 40፥4 ይመ። *አልተዋቸውም፤* ከ40፥27፤ 49፥14፤ 54፥8 ጋር ያነጻጽሩ።

42፥18 *ደንቈሮዎች ... ዕውሮች፤* 6፥10 እና ማብ ይመ።

42፥19 *አገልጋዬ፤* እስራኤልን ነው፤ የ41፥8-9 ማብ ይመ። *ከምልከው መልእክተኛዬስ፤* ከነቢያት ጋር የተያያዘ አባባል ነው (ሐጌ1፥13፤ ይመ፤ ከኢሳ44፥26፤ ሚል3፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

42፥21 *ሕጉን ታላቅና የተከበረ፤* በሲና ተራራ ላይ በአስፈሪ ሁኔታ (ዘፀ 34፥29) የተሰጠውን የሙሴ ሕግ የሚያመለክት ነው።

*42፥22 የተበዘበዘና የተዘረፈ፤* በአሦራውያንና (10፥6 እና ማብ ይመ) በባቢሎናውያን (39፥6) ለማለት ነው። *በጕድጓድ*

በወህኒ ቤት የተዘጋበት ነው፤
ተበዝብዘዋል፣
የሚያድናቸውም የለም፤
ተማርከዋል፣
“መልሷቸው” የሚልም የለም።

[23]ከእናንተ ይህን የሚሰማ፣
ለሚመጣውም ጊዜ አስተውሎ የሚያደምጥ
ማነው?
[24]ያዕቆብን ለዝርፊያ፣
እስራኤልን ለምርኮ የዳረገ ማነው?
በኀጢአት የበደልነው፣
*እግዚአብሔር* አይደለምን?
መንገዱን ለመከተል፣
ለሕጉም መታዘዝ አልፈለጉምና።
[25]ስለዚህ የሚነድ ቍጣውን፣
የጦርነትንም መዓት አፈሰሰባቸው፤
በእሳት ነበልባል ከበባቸው፤ እነርሱ ግን
አላስተዋሉም፤
አቃጠላቸው፤ እነርሱ ግን ልብ አላሉም።

## የእስራኤል ብቸኛ አዳኝ

**43** አሁን ግን፣ ያዕቆብ ሆይ! የፈጠረህ፤
እስራኤል ሆይ! የሠራህ፣
*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
“ተቤዥቼሃለሁና አትፍራ፤
በስምህ ጠርቼሃለሁ፤ አንተ የእኔ ነህ፤
[2]በውሃ ውስጥ በምታልፍበት ጊዜ፣
ከአንተ ጋር እሆናለሁ፤
ወንዙን ስትሻገረው፣
አያሰጥምህም፤
በእሳት ውስጥ ስትሄድ፣
አያቃጥልህም፤
ነበልባሉም አይፈጅህም።
[3]እኔ *እግዚአብሔር* አምላክህ፣
የእስራኤልም ቅዱስ መድኀኒትህ ነኝና፤
ግብፅን ለአንተ ቤዛ እንድትሆን፣
ኢትዮጵያንና ሳባን በአንተ ፈንታ እሰጣለሁ።
[4]ለዐይኔ ብርቅና ክቡርም ስለ ሆንህ፣
እኔም ስለምወድህ፣
ሰዎችን በአንተ ምትክ፣
ሕዝቦችንም በሕይወትህ ፈንታ እሰጣለሁ።
[5]ከአንተ ጋር ነኝና አትፍራ፤
ልጆችህን ከምሥራቅ አመጣለሁ፤
ከምዕራብም እሰበስብሃለሁ።
[6]ሰሜንን፣ ‘አምጣ’፣
ደቡብንም፣ ‘ልቀቅ’ እላለሁ፤
ወንዶች ልጆቼን ከሩቅ፣
ሴቶች ልጆቼንም ከምድር ዳርቻ፣
[7]በስሜ የተጠራውን ሁሉ፣
ለክብሬ የፈጠርሁትን፣
ያበጀሁትንና የሠራሁትን አምጡ።”

[8]ዐይን እያላቸው የታወሩትን፣
ጆሮ እያላቸው የደነቈሩትን አውጣ።
[9]ሕዝብ ሁሉ በአንድነት ይሰብሰብ፤
ሰውም ይከማች፤
ከእነርሱ አስቀድሞ ይህን የነገረን፣
የቀድሞውን ነገር ያወጀልን ማን ነው?
ሌሎችን ሰምተው፣ “እውነት ነው” እንዲሉ፣
ትክክለኝነታቸውም እንዲረጋገጥ
ምስክሮቻቸውን ያቅርቡ።
[10]“ታውቁና ታምኑብኝ ዘንድ፣
እርሱ እኔ እንደ ሆንሁ ትረዱ ዘንድ፣
እናንተ ምስክሮቼ፣

42፥23 ዘዳ32፥29፤ መዝ81፥13፤ ኢሳ47፥7፤ 48፥18፤57፥11
42፥24 ኢሱ1፥7፤ 2ነገ17፥6፤ መዝ119፥136፤ ኢሳ5፥24፤10፥5-6፤ 30፥15፤43፥28፤47፥6፤ ኤር44፥10
42፥25 2ነገ22፥13፤ 25፥9፤ ኢዮ40፥11፤ ኢሳ1፥3፤29፥13፤47፥7፤ 51፥17፤57፥1፡11፤ 66፥15፤ ኤር4፥4፤ 21፥12፤ ሰቆ2፥3፤ ሕዝ7፥19፤ ሆሴ7፥9፤ ናሆ1፥6
43፥1 ቍ7፤ ዘፍ2፥7፤32፥28፤ ዘፀ6፥6፤ ዘዳ7፥6፤ ኢዮ19፥25፤ ኢሳ27፥11፤42፥6፤ 44፥21፤45፥3-4፤ 49፥1፤ ሚል3፥17
43፥2 ዘፍ26፥3፤ ዘፀ14፥22፤ መዝ66፥12፤ ኢሳ8፥7፤29፥6፤30፥27፤ ዳን3፥25-27
43፥3 ዘፍ10፥7፤ ዘፀ14፥30፤20፥2፤ መሳ2፥18፤ መዝ3፥8፤ 68፥31፤ ምሳ21፥18፤ ኢሳ19፥1፤20፥3፤25፥9፤ 41፥20፤ ሕዝ29፥20
43፥4 ዘፀ19፥5፤ ኢሳ49፥5፤63፥9፤ ራእ3፥9
43፥5 ዘፍ15፥1፤ 21፥22፤ ዘፀ14፥22፤ ኢሳ11፥12፤24፥14፤ 41፥8፤44፥2፤49፥18፤ 54፥3፤61፥9፤66፥22፤ ኤር30፥10-11፤ ዘካ8፥7፤ ማቴ8፥11
43፥6 ዘዳ30፥4፤ መዝ107፥3፤ ኤር23፥8፤ ሕዝ16፥61፤36፥24፤ 2ቆሮ6፥18
43፥7 ቍ1፡21፤ መዝ86፥9፤100፥3፤ ኢሳ19፥25፤ 27፥11፤ 48፥1፤56፥5፤62፥2፤63፥19፤ 65፥1፤ ኤር15፥16፤ ያዕ2፥7
43፥8 ኢሳ 6፥9-10፤42፥20፤ ሕዝ12፥2
43፥9 ኢሳ41፥1፡ 26፤45፥20፤48፥14
43፥10 ቍ11፡12፤ ዘፀ6፥7፤ ዘዳ4፥35፤ 32፥39፤ ኢሱ24፥22፤ መዝ 86፥10፤ ኢሳ19፥21፤20፥3፤ 41፥8-9፤44፥6፡8፤45፥5-6፡14፤ ኤር14፥22

---

ውስጥ የተጠመደበት፣ በወህኒ ቤት፤ ቍ7 እና ማብ ይመ፤ ከምሳ6፥2-4 ጋር ያነጻጽሩ።

42፥24 *ያዕቆብን ... የዳረገ ማነው?* ባቢሎናውያን እስራኤላውያንን ያሸነፏቸው አማልክታቸው ከእውነተኛው አምላክ ከእግዚአብሔር ይልቅ ብርቱ ሆነው ሳይሆን (40፥17-18፤ 1ነገ20፥23 ይመ)፣ እግዚአብሔር ሕዝቡን መቅጣት ስለ ፈለገ ብቻ ነበር።

42፥25 *ቍጣውን ... አፈሰሰባቸው፤* እስራኤል የጌታን ቀን አስቀድማ ቀምሳዋለች (5፥25፤ 9፥12፡17፡21፤ 13፥3፤ 34፥2 እና ማብ ይመ፤ ከኤር10፥25 ጋር ያነጻጽሩ)።

43፥1 *የፈጠረህ፤ ... የሠራህ፤* እግዚአብሔር የመጀመሪያውን ሰው እንደ ፈጠረ የእስራኤልን ሕዝብ ፈጥሮአል (ዘፍ1፥27፤ ኢሳ 43፥7፡15፡21፤ 44፥2፡24 ይመ)። *አትፍራ፤* 41፥10 እና ማብ ይመ። *ተቤዥቼሃለሁና፤* የ35፥9፤ 41፥14 እና ማብ ይመ። ግሡ በ29፥22፤ 44፥22-23፤ 48፥20 ተጠቅሶአል (ከዘፀ 15፥3 ጋር ያነጻጽሩ)። *በስምህ ጠርቼሃለሁ፤* በተለየ መንገድ እንዲያገለግሉት እግዚአብሔር እስራኤልን ጠራ (ስለ ቂሮስ በ45፥3-4 የተነገረውን ይመ)፤ ዘፀ31፥2፤ 35፥30 ይመ።

*43፥2 በውሃ ... ወንዙን፤* ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ ቀይ ባሕርንና (ዘፀ14፥21-22) የዮርዳኖስን ወንዝ (ኢሱ 3፥14-17) የተሻገሩበትን ሁኔታ ለማመልከት ይሆናል፤ ከመዝ 66፥6፡12 ጋር ያነጻጽሩ። *በእሳት ውስጥ ስትሄድ፤* ሲድራቅ፣ ሚሳቅና አብድናጎ በእሳት መካከል በተጣሉ ጊዜ እግዚአብሔር እሳቱ እንዳይፈጃቸው ያደረገውን ታምራት የሚያመለክት ነው (ዳን3፥25-27)፤ ከ42፥25 ጋር ያስተያዩ።

43፥3 *የእስራኤልም ቅዱስ፤* የ1፥4፤ 41፥14 ማብ ይመ። *መድኀኒትህ፤* ከግብፅ ወይም ከባቢሎን ጭቈና እንዲሁም በኀጢአት ምክንያት ከሚመጣው መንፈሳዊ ጭቈና ነጻ ማውጣትን የሚያመለክት ነው (19፥20 እና ማብ፤ 25፥9 እና ማብ፤ 33፥22፤ 35፥4 እና ማብ 43፥11-12፤ 45፥15፡21-22፤ 49፥25፤ 60፥16፤ 63፥8-9 ይመ)። “ኢሳይያስ” ማለት እግዚአብሔር ያድናል ማለት ነው። *ቤዛ፤* ፋርሶች ግብፅን፣ ኢትዮጵያንና ሳባን አሸንፈዋል፤ ምናልባትም ይህን ድል ያገኙት ለእስራኤላውያን የበጎነት ሥራ ስለ ሠሩላቸው ሊሆን ይችላል (የ41፥2 ማብ ይመ)፤ ከሕዝ 29፥19-20 ጋር ያነጻጽሩ። *ኢትዮጵያንና፤* የ18፥1 ማብ ይመ። *ሳባ፤* ከኢትዮጵያ አጠገብ ያለ ምድር ነው (ከ45፥14 ጋር ያነጻጽሩ፤ መዝ72፥10 ይመ)፤ ምናልባትም በደቡብ ዐረቢያ ክፍል የሚገኘው ሳባ እየተባለ የሚጠራው ሳይሆን አይቀርም (ዘፍ10፥7 እና ማብ ይመ፤ ሕዝ27፥21-22 ይመ)፤ ወይም ከቀይ ባሕር ማዶ በአፍሪካ የሚገኘው የኢትዮጵያ ምድር ሊሆን ይችላል።

43፥5 *አትፍራ፤* 41፥10 እና ማብ ይመ። *ከምሥራቅ፤* በተለይ አሦርና ባቢሎን ለማለት ነው፤ 11፥11-12 እና ማብ ይመ፤ ከመዝ 107፥3 ጋር ያነጻጽሩ። *ከምዕራብም፤* ለምሳሌ የ11፥11 ደሴቶች ናቸው (24፥14-15፤49፥12 ይመ)።

43፥6 *ሰሜንን፤* ለምሳሌ ሐማት (10፥9 እና ማብ 11፥11 ይመ) ነው። *ደቡብንም፤* ግብፅን ማለት ነው። *ከምድር ዳርቻ፤* የ11፥12 ማብ ይመ (ከ41፥5፤ 42፥10 ጋር ያነጻጽሩ)።

43፥7 *በስሜ የተጠራውን፤* የእግዚአብሔርን ሕዝብ የሚያመለክት ነው። *የፈጠርሁትን፣ ... የሠራሁትን፤* ቍ1 እና ማብ ይመ።

43፥8 *የታወሩትን ... የደነቈሩትን፤* ምናልባት እስራኤልን የሚያመለክት ይሆናል (6፥10 እና ማብ 42፥18-20 ይመ)።

*43፥9-13፤* የፍርድ ቤትን ችሎት ያመለክታል፤ 41፥21-22 ይመ።

43፥9 *ሕዝብ ... ሰውም ይከማች፤* 41፥1 እና ማብ ይመ። *አስቀድሞ ... የነገረን፤* 41፥26 እና ማብ ይመ። *የቀድሞውን ነገር፤* 41፥22 እና ማብ ይመ። *ምስክሮቻቸውን፤* በአማልክት ወይም በአምላኪዎቻቸው የተነገረውን ለማረጋገጥ ነው (41፥26 ይመ)።

43፥10 *እናንተ ምስክሮቼ፤* ቍ12፤44፥8 ይመ። እግዚአብሔር ስለ እስራኤል ሲል ያደረገው የቸርነቱ ሥራ የማዳን ኀይሉ

የመረጥሁትም ባሪያዬ ናችሁ" ይላል
እግዚአብሔር።
"ከእኔ በፊት አምላክ አልተሠራም፤
ከእኔም በኋላ አይኖርም።
[11]እኔ፣ እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤
ከእኔም ሌላ የሚያድን የለም።
[12]ገልጫለሁ፤ አድኛለሁ፤ ተናግሬአለሁ፤
በመካከላችሁ እኔ እንጂ ባዕድ አምላክ
አልነበረም።
እኔ አምላክ እንደ ሆንሁ፣
እናንተ ምስክሮቼ ናችሁ" ይላል እግዚ
አብሔር፤
[13]"ከጥንት ጀምሮ እኔው ነኝ፤
ከእጄም ማውጣት የሚችል የለም፤
እኔ የምሠራውን ማን ማገድ ይችላል?"

### የእግዚአብሔር ምሕረትና የእስራኤል አለመታመን

[14]የእስራኤል ቅዱስ፣
የሚቤዣችሁ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"ስለ እናንተ በባቢሎን[x] ላይ ሰራዊት እሰዳለሁ፤
በሚመኩባቸውም መርከቦች፣
ባቢሎናውያንን ሁሉ እንደ ኰብላይ
አመጣለሁ።
[15]እኔ እግዚአብሔር፣ የእናንተ ቅዱስ፣
የእስራኤል ፈጣሪ፣ ንጉሣችሁ ነኝ።"

[16]በባሕር ውስጥ መንገድ፣
በማዕበል ውስጥ መተላለፊያ ያበጀ፣
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
[17]እንደ ገና ላይነሡ እዚያው እንዲተኙ፣
እንደ ጧፍ ኵስታሪ ረግፈው እንዲጠፉ፣
ሠረገሎችንና ፈረሶችን፣
ሰራዊቱንና ደጀኑን በአንድነት ያወጣ እንዲህ
ይላል፤
[18]"የቀደመውን ነገር አታስቡ፤
ያለፈውን እርሱ።
[19]እነሆ፤ አዲስ ነገር አደርጋለሁ፤
እርሱም አሁን ይበቅላል፤ አታስተውሉትምን?
በምድረ በዳም መንገድ አዘጋጃለሁ፤
በበረሓም ምንጭ አፈልቃለሁ፤
[20]የምድረ በዳ አራዊት፣
ቀበሮና ጕጕት ያከብሩኛል፤
በምድረ በዳ ውሃ፣
በበረሓም ምንጭ እሰጣለሁና።
ለመረጥሁት ሕዝቤ ውሃ እሰጣለሁ፤
[21]ለራሴ ያበጀሁት ሕዝብ
ምስጋናዬን ያውጅ ዘንድ ይህን አደርጋለሁ።

[22]"ያዕቆብ ሆይ፤ አንተ ግን አልጠራኸኝም፤
እስራኤል ሆይ፤ የእኔ ነገር ታክቶሃል።
[23]ለሚቃጠል መሥዋዕት በጎች አላመጣህልኝም፤
በመሥዋዕትህም አላከበርኸኝም።
በእህል ቍርባን አላስቸገርሁህም፤
በዕጣን መሥዋዕትም አላሰለቸሁህም።
[24]መልካም መዐዛ ያለው ዕጣን አልገዛህልኝም፤
በመሥዋዕትህ ሥብ አላጠገብኸኝም፤
ነገር ግን የኀጢአት ሸክምህን ጫንህብኝ፤
በበደልህም አደከምኸኝ።

[25]"ስለ ራሴ ስል መተላለፍህን የምደመስስልህ፣
እኔ፣ እኔው ነኝ፤
ኀጢአትህን አላስባትም።
[26]እስቲ ያለፈውን አስታውሰኝ፤
ተቀራርበን እንከራከርበት፤
ትክክለኛ ስለ መሆንህም አስረዳ።
[27]የመጀመሪያው አባትህ ኀጢአት ሠርቶአል፤
መምህሮችህም ዐመፁብኛል።

ኢሳ11፥12፤60፥4፤
43፥11 ቍ10፤ ዘፀ6፥2፤መዝ3፥8፤ 18፥31፤ኢሳ25፥9፤ 42፥8፤64፥4
43፥12 ቍ10፤ ዘዳ32፥12
43፥13 ዘኍ23፥8፤ ዘዳ32፥39፤ኢዮ9፥12፤ መዝ90፥2፤ኢሳ46፥4፤ 48፥12
43፥14 ዘፀ15፥13፤ ኢዮ19፥25፤ኢሳ1፥4፤ 13፥14-15፤23፥13፤ 41፥20
43፥15 ኢሳ27፥11፤ 41፥21፤42፥8፤45፥11
43፥16 ዘፀ14፥29፤ 15፥8፤ኢሳ11፥15
43፥17 ዘፀ14፥9፡22፤ ኢዮ13፥25፤ መዝ76፥5-6፤118፥12፤ ኢሳ1፥31፤ኤር51፥21፤ ሕዝ38፥4
43፥18 ኢሳ41፥22
43፥19 መዝ126፥4፤ ኢሳ33፥21፤35፥7፤ 40፥3፤41፥22፤ ኤር16፥14-15፤ 23፥7-8፤2ቆሮ5፥17፤ ራእ21፥5
43፥20 ዘኍ20፥8፤ መዝ148፥10፤ኢሳ13፥22
43፥21 ቍ7፤ ዘፍ2፥7፤መዝ66፥2፤ 102፥18፤ሚል3፥17፤ 1ጴጥ2፥9
43፥22 ኢሉ22፥5፤ ኢሳ1፥14፤30፥11
43፥23 ዘፀ29፥41፤ 30፥35፤ዘሌ2፥1፤ ኤር7፥22፤አሞ5፥25፤ ሚክ6፥3፤ዘካ7፥5-6፤ ሚል1፥6-8፡12-13
43፥24 ዘፀ30፥23፤ ዘሌ3፥9፤ኢሳ1፥14፤ 7፥13፤ኤር8፥21፤ 44፥22፤ሚል2፥17
43፥25 2ሳሙ12፥13፤ ኢሳ37፥35፤38፥17፤64፥9፤ሕዝ20፥44፤ሚክ7፥18፤ማር2፥7፤ ሉቃ5፥21፤ሐሥ3፥19 43፥26 ኢሳ1፥18፤ 41፥1፤49፥25፤50፥8
43፥27 ዘፍ12፥18፤ኢሳ9፥15፤24፥20፤ 28፥7፤48፥8፤ኤር5፥31

[x]14 ወይም፣ *ከለዳውያን* ማለት ነው።

ማረጋገጫ ነው። *ባሪያዬ፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ።

*43፥11፤* ዋና ሐሳቡ በ44፥6፡8፤ 45፥5-6፡18፡21-22፤ 46፥9 ተደጋግሞ ተጠቅሶአል (ዘዳ32፥39 ይመ)። *የሚያድን፤* ቍ3 እና ማብ ይመ።

43፥12 *ባዕድ አምላክ፤* ከዘዳ32፥12፡16 ጋር ያነጻጽሩ። እስ ራኤላውያን ባዕዳን አማልክትን በተደጋጋሚ አምልከዋል (መሳ2፥12-13 ይመ)። *ምስክሮቼ፤* ቍ10 እና ማብ ይመ።

*43፥13፤* ቍ11 ይመ። *ከእጄም ማውጣት የሚችል የለም፤* በዘዳ32፥39 ላይ የተጠቀሰ ዐቢይ ሐሳብ ነው።

43፥14 *የእስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4፤ 41፥14 እና ማብ ይመ። *የሚቤዣችሁ፤* 41፥14 እና ማብ ይመ። *ባቢሎን፤* የ13፥1 ማብ ይመ። *መርከቦች... እንደ ኰብላይ፤* ባቢሎናውያን የፋርስን ባሕረ ሰላጤ እንዲሁም የኤፍራጥስንና የጤግሮስን ወንዞች ለንግድ ሥራ ተጠቅመውባቸዋል። ነገር ግን ውብና ታላላቅ የሆኑት መርከቦቻቸው (ከ2፥16 ጋር ያነጻጽሩ) አንድ ቀን ሸሽቶ ለማምለጥ ያገለግሏቸዋል ማለት ነው (ከኤር51፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

43፥15 *ፈጣሪ፤* ቍ1 እና ማብ ይመ። *ንጉሣችሁ፤* እግዚ አብሔር የይሹሩን ንጉሥ (የእስራኤል) በሚል ስም በዘዳ33፥5 ላይ ተጠርቶአል (ከ1ሳሙ8፥7 ጋር ያስተያዩ)።

*43፥16-17፤* ቀይ ባሕርን ሲሻገሩ የነበረውን ሁኔታ ያመለክታል (ቍ2 እና ማብ ይመ)። የእስራኤል አምላክ በተዋጋቸው ጊዜ የፈርዖን ሠረገሎችና ፈረሰኞች ተደምስሰዋል (51፥10፤ ዘፀ14፥28፤ 15፥4 ይመ)።

43፥17 *እንደ ጧፍ ኵስታሪ ረግፈው እንዲጠፉ፤* ከ42፥3 ጋር ያስተያዩ።

43፥19 *አዲስ ነገር፤* 42፥9 እና ማብ ይመ። *በምድረ በዳም መንገድ፤* 35፥8፤ 40፥3 እና ማብ ይመ። *በበረሓም ምንጭ፤* ቍ20፤ 32፥2 እና ማብ ይመ። ከ42፥15 ማብ ጋር ያስተያዩ። 40፥20 *ቀበሮና ጕጕት፤* የምድረ በዳ እንስሳት ናቸው (13፥21-22፤ 34፥13-15፤ 35፥7 ይመ)።

43፥21 *ሕዝብ ምስጋናዬን ያውጅ ዘንድ፤* ከ42፥12 ጋር ያነጻጽሩ።

*43፥22-24፤* እስራኤላውያን መሥዋዕት አምጥተው ይሆናል (1፥11-15 እና ማብ ይመ)፤ ነገር ግን ልባቸው ከእግዚ አብሔር እጅግ የራቀ ነበር።

43፥22 *አልጠራኸኝም ... ታክቶሃል፤* ጸሎታቸው በተከፈለ ልብ ይደረግ እንደ ነበር ግልጽ ነው (ከመዝ 69፥3 ጋር ያስተያዩ)።

43፥23 *አላስቸገርሁህም ... አላሰለቸሁህም፤* እግዚአብሔር ሕዝቡን ችግር ላይ የሚጥል ከሕዝቡ ዐቅም በላይ የሆነ ነገር አልጠየቀም።

43፥24 *መዐዛ ያለው ዕጣን፤* ልዩ ዕጣን ነው (ቍ23 ይመ)፤ በማሕ 4፥14፤ ኤር6፥20 ተጠቅሶአል። *ሥብ፤* የ34፥6 ማብ ይመ። *ሸክምህን ጫንህብኝ ... አደከምኸኝ፤* 1፥14 ይመ።

43፥25 *መተላለፍህን የምደመስስልህ፤* እስራኤላውያን በኀጢአታቸው መቀጣት የሚገባቸው ቢሆኑም (ቍ28)፣ እግዚ አብሔር ምን ጊዜም ሕዝቡን ይቅር ለማለት ዝግጁ ነው (1፥18፤ 44፥22ይመ፤ 40፥2 እና ማብ ይመ)።

43፥26 *አስረዳ፤* እግዚአብሔር በ41፥21-22 ላይ በአሕዛብ እንዳደረገው ሁሉ አሁንም እስራኤልን በፍርድ ወንበር ፊት ያቀርበዋል።

43፥27 *የመጀመሪያው አባትህ፤* 51፥2 ይመ። አብርሃምም እንኳ ቢሆን ኀጢአተኛ ነበር (ዘፍ12፥18፤ 20፥9 ይመ)። *መምህሮችህም፤* ምናልባት ነቢያቱንና ካህናቱን ለማመልከት ሳይሆን አይቀርም።

[28]ስለዚህ የመቅደስህን አለቆች አዋርዳለሁ፤
ያዕቆብን ለጥፋት፣[†]
እስራኤልን ለስድብ እዳርጋለሁ።

### የተመረጠው እስራኤል

**44** "ነገር ግን አሁንም ባሪያዬ ያዕቆብ፣
የመረጥሁህ እስራኤል ሆይ፣ ስማ፤
[2]የፈጠረህ፣ በማሕፀን የሠራህ፣
የሚረዳህ፣
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
ባሪያዬ ያዕቆብ፣
የመረጥሁህ ይሹሩን ሆይ፣ አትፍራ።
[3]በተጠማ ምድር ላይ ውሃ፤
በደረቅ መሬት ላይ ወንዞችን አፈሳለሁና፤
መንፈሴን በዘርህ፣
በረከቴንም በልጅ ልጅህ ላይ አወርዳለሁ።
[4]እነርሱም በለመለመ መስክ ላይ እንደ ሣር፣
በወንዝ ዳር እንደ አኻያ ዛፍ ይበቅላሉ።
[5]አንዱ፣ 'እኔ *የእግዚአብሔር ነኝ*' ይላል፤
ሌላው ራሱን በያዕቆብ ስም ይጠራል
ሌላው ደግሞ በእጁ ላይ '*የእግዚአብሔር ነኝ*'
ብሎ ይጽፋል፤
ራሱን በእስራኤል ስም ይጠራል።

### አምላክ እግዚአብሔር ብቻ ነው

[6]"የእስራኤል ንጉሥና ቤዛ እግዚአብሔር፣
የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
የፊተኛውም እኔ ነኝ፤ የኋለኛውም እኔ ነኝ፤
ከእኔ በቀር ሌላ አምላክ የለም።
[7]እስቲ እንደ እኔ ማን አለ? ይናገር፤
ሕዝቤን ከጥንት ስመሠርት ምን እንደ ነበረ፣
ገና ወደ ፊት ምን እንደሚሆን፣
ይናገር፤ በፊቴ ያስረዳ፤
ስለሚመጣውም ነገር አስቀድሞ ይናገር።
[8]አትፍሩ፤ አትደንግጡ፤
ይህን አልነገርኋችሁምን? ቀድሞስ አላሳወ
ቅኋችሁምን?
ለዚህ እናንተ ምስክሮቼ ናችሁ። ከእኔ በቀር
ሌላ አምላክ አለን? ፈጽሞ!
ወይም ሌላ ዐለት አለ? የለም! ማንንም
አላውቅም።"

[9]ጣዖት የሚሠሩ ሁሉ ከንቱዎች፣
የሚሠሩባቸውም ነገሮች ዋጋ ቢስ ናቸው፤
የሚናገሩላቸው ዕውሮች ናቸው፤
ዕውቀት የላቸውም ያፍራሉም።
[10]ለምንም የማይጠቅመውን አምላክ የሚቀርጽ፣
ጣዖትን የሚያበጅስ ማነው?
[11]ጣዖት የሚሠራ ሰው እንጂ ሌላ አይደለም፤
እርሱና መሰሎቹም ያፍራሉ፤
ሁሉም ተሰብስበው በአንድ ላይ ይቁሙ፤
ይደነግጣሉ፤ ይዋረዳሉም።
[12]ብረት ቀጥቃጭ መሥሪያን ይይዛል፤
በከሰል ፍም ላይ ይሠራዋል፤
ጣዖትን በመዶሻ ቅርጽ ይሰጠዋል፤
በክንዱም ኀይል ያበጀዋል።
ከዚያም ይራባል፤ ጕልበት ያጣል፤
ውሃ ይጠማል፤ ይደክማል።
[13]ጠራቢ በገመድ ይለካል፤
በጠመኔ ንድፍ ያወጣል፤
በመሮ ይቀርጸዋል፤
በድርከል ምልክት ያደርግበታል።
በሰው አምሳል ይቀርጸዋል፤
የሰውንም ውበት ያለብሰዋል፤
በማምለኪያም ስፍራ ያስቀምጠዋል።
[14]ዝግባ ይቈርጣል፤
ሾላ ወይም ዋንዛ ይመርጣል፤
በደን ውስጥ ካሉት ዛፎች ጋር እንዲያድግ
ይተወዋል፤
ወይም ጥድን ይተክላል፤ ያንንም ዝናም
ያሳድገዋል።

2ዜና6፥21፤ኢዮ7፥21፤
43፥28 ዘኍ5፥27፤ ዘዳ13፥15፤መዝ39፥8፤ ኢሳ42፥24፤ኤር24፥9፤ ዘካ5፥3፤ሕዝ5፥15
44፥1 ቍ21፤ ዘፍ16፥11፤ኢሳ14፥1
44፥2 ቍ21፤ ዘፍ2፥7፤ዘኍ23፥21፤ ዘዳ32፥15፤መዝ139፥ 13፤149፥2፤ኢሳ27፥11፤ 41፥10፤43፥5፤ ኤር30፥10፤46፥27
44፥3 ምሳ9፥5፤ ኢሳ11፥2፤32፥2፤35፥7፤ 61፥9፤65፥23፤ ሕዝ36፥27፤ ኢል3፥18፤ሚል3፥10፤ ማር1፥8፤ዮሐ4፥10፤ ሐሥ2፥17
44፥4 ዘሌ23፥40፤ ኢዮ5፥25፤40፥22፤ መዝ72፥16፤
44፥5 ዘፀ13፥9፤ መዝ116፥16፤ ኢሳ19፥21፤60፥3፤ 66፥23፤ኤር50፥5፤ ዘካ8፥20-22፤13፥9፤ 14፥16
44፥6 ዘዳ6፥4፤ 1ዜና17፥20፤ ኢዮ19፥25፤ መዝ18፥31፤ኢሳ41፥4፤ 41፥21፤43፥1:10፤ ራእ1፥8:17
44፥7 ዘዳ32፥39፤ ኢሳ41፥22:26
44፥8 ዘፍ49፥24፤ ኢሳ40፥21፤42፥9፤ 43፥10
44፥9 ዘፀ20፥4፤ ዘሌ19፥4፤ኢሳ1፥29፤ 26፥11፤40፥19፤ 41፥24፤65፥13፤66፥5፤ ኤር22፥22
44፥10 ኢሳ40፥19፤ 41፥29፤ኤር10፥5፤ ሐሥ19፥26
44፥11 ቍ9፤ 2ነገ19፥18፤ ኢሳ1፥29፤ 37፥19
44፥12 ኢሳ40፥19: 54፥16፤ሐሥ17፥29 44፥13 መሳ17፥4-5፤መዝ115፥4-7፤ኢሳ41፥7
44፥14 ኢሳ41፥19

[†]28 የዕብራይስጡ ቃል አንድን ሰው ወይም ነገር ሙሉ በሙሉ በማጥፋት ለእግዚአብሔር መስጠትን ያመለክታል።

43፥28 *ለጥፋት ... አደርጋለሁ፤* ሙሉ በሙሉ ማጥፋት ለማለት ነው፤ የ34፥2 ማብ ይመ። ማንኛውም የእስራኤል ከተማ አምልኮ ጣዖትን ካስተናገደ ዕጣ ፈንታው ይኸው ነው (ዘዳ13፥12-15)። በጣዖት አምልኮ ምክንያት (ሕዝ7፥15-22) ኢየሩሳሌም ባቢሎናውያን ብዙ መከራ አድርሰውባታል (2ነገ25፥8-9 ይመ)።

44፥1-2 *ባሪያዬ፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ።

44፥2 *የፈጠረህ፤* 43፥1 እና ማብ ይመ። *በማሕፀን፤* ቍ24 ይመ። የፈጣሪ ርኅራኄ እዚህ ላይ ተገልጦአል (49፥5፤ ኤር1፥5 ይመ)። *አትፍራ፤* ቍ8፤ 41፥10 እና ማብ ይመ። *ይሹሩን፤* እስራኤልን ለማለት ነው (ቍ1 ይመ)፤ በሌላ ስፍራ ላይ የሚገኘው በዘዳ32፥15 ብቻ ነው፤ ትርጓሜውም ቀጥተኛው ወይም "እስራኤል" ማለት ነው፤ 33፥5:21 ይመ።

44፥3 *ውሃ ... ወንዞችን፤* 30፥25፤ 32፥2፤ 35፥6-7 እና ማብ 41፥18 ይመ። *መንፈሴን ...አወርዳለሁ፤* በ32፥15 ላይ ከተገለጸውና በኢል2፥28 ላይ ከተጠቀሰው ከመሲሑ ዘመን ጋር የተያያዘ ነው።

44፥4 *ሣር፤* በ35፥7 ከተለመደው ልምላሜ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ምሳሌ ነው (ከ37፥27፤ 40፥6-8 ጋር ያስተያዩ)።

44፥5 *በ ... ስም ይጠራል፤* ከእግዚአብሔር ሕዝብ ከያዕቆብ ጋር ለማዛመድ ነው፤ 43፥7 እና ማብ ይመ። *በእጁ ላይ ... ይጽፋል፤* ምናልባት የባለቤትነት ምልክት (ከ49፥16፤ ራእ13፥16 ጋር ያነጻጽሩ) ወይም የማንነት መለያ ማስታወሻ ሳይሆን አይቀርም (ከዘፀ 13፥9:16 ጋር ያነጻጽሩ)።

44፥6 *ንጉሥ፤* 43፥15 እና ማብ ይመ። *ቤዛ፤* ቍ24:41፥14 እና ማብ ይመ። *የፊተኛውም ... ኋለኛውም፤* 41፥4 እና ማብ ይመ። *ከእኔ በቀር ሌላ አምላክ፤* 43፥11 እና ማብ ይመ።

44፥7 *ስለሚመጣውም ...ይናገር፤* 41፥22:26 እና ማብ ይመ።

44፥8 *እናንተ ምስክሮቼ ናችሁ፤* 43፥10 እና ማብ ይመ። *ዐለት፤* 17፥10 እና ማብ ይመ። በቍ2 እና በ43፥11-13 ኢሳይያስ ከሙሴ መዝሙር በመነሣት እግዚአብሔርን "ዐለት" በማለት ይገልጸዋል (ዘዳ 32፥4፥15፥30-31)፤ አባባሉ በመዝሙረ ዳዊትም ውስጥ ተደጋግሞ ይታያል (መዝ18፥2 እና ማብ ይመ)።

*44፥9-20፤* የጣዖት አምልኮን ከንቱነት የሚገልጽ ፌዝ (40፥18-20 እና ማብ ይመ)።

44፥9 *ከንቱዎች ...ዋጋ ቢስ፤* እንደ አሕዛብና እንደ ጣዖቶቻቸው ማለት ነው (40፥17፤ 41፥24 እና ማብ ይመ)። *ያፍራሉም፤* ከቍ11፤ 42፥17፤ 45፥16 ጋር ያነጻጽሩ)

44፥11 *ጣዖት የሚሠራ፤* 40፥19 እና ማብ ይመ።

*44፥12-20፤* ሁለት የጣዖት ምስሎች ተገልጸዋል፤ እነዚህም በቍ12 ላይ የብረት፣ ከቍ13-20 ላይ የዕንጨት ምስል ናቸው። ከዕንጨት ተጠርቦ የሚሠራ የጣዖት ምስልን ማበጀት ይበልጥ የተለመደ ነበር (40፥20 ይመ)

44፥12 *ይደክማል፤* እግዚአብሔር ግን ፈጽሞ አይደክምም (40፥28)።

44፥13 *በሰው አምሳል፤* ሰው በእግዚአብሔር አምሳል ተፈጥሮአል (ዘፍ1፥26-27 እና ማብ ይመ)፤ ጣዖት የሚሠራው ግን በሰው አምሳል ነው (ዘዳ4፥16፤ ሮሜ1፥23)።

44፥14 *ዝግባ ... ሾላ ወይም ዋንዛ፤* በዚያ ዘመን እጅግ ውድ የሆኑ ዛፎች ናቸው፤ 9፥10፤ 41፥19 እና ማብ ይመ።

15ሰው ለማገዶ ይጠቀምበታል፤
ከዚያም ጥቂት ወስዶ በማንደድ ይሞቀዋል፤
እንጀራም ይጋግርበታል::
ከዚሁ ጠርቦ አምላክ ያበጃል፤
ያመልከዋል፤
ጣዖትን ይሠራል፤ ወድቆም ይሰግድለታል::
16ግማሹን ዕንጨት ያነደዋል፤
በላዩ ምግቡን ያበስልበታል፤
ሥጋ ጠብሶበት እስኪጠግብ ይበላል፤
እሳቱን እየሞቀ እንዲህ ይላል፤
"እሰይ ሞቀኝ፤ እሳቱም ይታየኛል::"
17በቀረው ዕንጨት የጣዖት አምላኩን ይሠራበታል፤
ወድቆ ይሰግድለታል፤ ያመልከዋል፤
ወደ እርሱም እየጸለየ፣
"አንተ አምላኬ ነህ፤ አድነኝ" ይላል::
18ምንም አያውቁም፤ አያስተውሉም፤
እንዳያዩ ዐይናቸው ተሸፍኖአል፤
እንዳያስተውሉ ልባቸው ተዘግቶአል::
19ማንም ቆም ብሎ አያስብም፤
ዕውቀት ወይም ማስተዋል ስለሌለው
እንዲህ ማለት አልቻለም፤
"ግማሹን በእሳት አቃጥዬዋለሁ፤
በፍሙ እንጀራ ጋግሬበታለሁ፤
ሥጋ ጠብሼበት በልቻለሁ፤
ታዲያ፣ በቀረው እንዴት ጸያፍ ነገር
እሠራለሁ?
ለግንድስ መስገድ ይገባኛልን?"
20ዐመድ ይቅማል፤ ተታላይ ልብ አስቶታል፤
ራሱን ለማዳን አይችልም፤
"ይህ በቀኝ እጄ ያለው ነገር ሐሰት
አይደለምን?"
ለማለት አልቻለም::

21"እስራኤል ሆይ፤ ባሪያዬ ነህና፣
ያዕቆብ ሆይ፤ ይህን አስብ::
እኔ ሠርቼሃለሁ፤ አንተም ባሪያዬ ነህ፤
እስራኤል ሆይ፤ አልረሳህም::
22መተላለፍህን እንደ ደመና፣
ኀጢአትህን እንደ ማለዳ ጭጋግ ጠርጌ
አስወግጃለሁ፤
ተቤዥቼሃለሁና
ወደ እኔ ተመለስ::"

23ሰማያት ሆይ፤ እግዚአብሔር ይህን
አድርጎአልና ዘምሩ፤
የምድር ጥልቆች ሆይ፤ በደስታ ጩኹ::
እናንት ተራሮች፣
እናንት ደኖችና ዛፎቻችሁ ሁሉ እልል በሉ፤
እግዚአብሔር ያዕቆብን ተቤዥቶአል፣
በእስራኤልም ክብሩን ገልጦአልና::

## ኢየሩሳሌም የሰው መኖሪያ ትሆናለች

24"ከማሕፀን የሠራህ፣ የተቤዠህም፣
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

ሁሉን ነገር የፈጠርሁ፣
ብቻዬን ሰማያትን የዘረጋሁ፣
ምድርን ያንጣለልሁ፣
እኔ እግዚአብሔር ነኝ::
25የሐሰተኞችን ነቢያት ምልክቶች አከሽፋለሁ፤
ሟርተኞችን አነሆልላለሁ፤
የጥበበኞችን ጥበብ እገለባብጣለሁ፤
ዕውቀታቸውንም ከንቱ አደርጋለሁ::
26የባሪያዎቼን ቃል እፈጽማለሁ፤
የመልእክተኞቼን ምክር አጸናለሁ::

ኢየሩሳሌምን 'የሰው መኖሪያ ትሆኛለሽ'፣
የይሁዳ ከተሞችንም፣ 'ይታነጻሉ'፣
ፍርስራሻቸውን፣ 'አድሳለሁ' እላለሁ::
27ጥልቁን ውሃ፣ 'ደረቅ ሁን፤

28፥41፥6-7፤
44፥15 ቊ19፤ ዘፀ20፥5፤2ዜና25፥14፤ ራእ9፥20
44፥16 ኢሳ47፥14
44፥17 ዘፀ20፥5፤ መሳ10፥14፤ 1ነገ18፥26፤ኢሳ2፥8፤ 45፥20፤46፥7፤47፥15፤ ኤር1፥16
44፥18 ኢሳ1፥3፤ 6፥9-10፤16፥12፤ 29፥10፤ኤር4፥22፤ 10፥8:14-15
44፥19 ቊ15:18-19፤ ዘዳ27፥15፤ኢሳ5፥13፤ 27፥11፤40፥20፤45፥20
44፥20 ዘዳ4፥28፤ ኢዮ15፥31፤መዝ102፥9፤ ኢሳ59፥3:4:13፤ ኤር9፥3፤10፥14፤ 51፥17፤ሆሴ10፥5፤ 13፥2፤ሮሜ1፥21-23: 25:28፤2ተሰ2፥11፤ 2ጢሞ3፥13
44፥21 መዝ27፥10፤ 136፥22፤ኢሳ27፥11፤ 43፥1፤46፥8፤49፥15፤ ኤር31፥20፤ዘካ10፥9
44፥22 2ሳሙ12፥13፤ 2ዜና6፥21፤ኢዮ22፥23፤ ኢሳ33፥24፤45፥22፤ 55፥7፤ኤር36፥31 ሚል3፥7፤ማቴ20፥28፤ ሐሥ3፥19፤1ቆሮ6፥20
44፥23 ዘፀ6፥6፤ 16፥7፤ዘሌ10፥3፤ 1ዜና16፥31፤ መዝ65፥13፤98፥4:8፤ 148፥7፤ኢሳ4፥2፤ 12፥6፤43፥7፤46፥13፤ 49፥3፤51፥11፤ 52፥1፤55፥5፤60፥9:21፤ 61፥3፤62፥12፤ ኤር30፥19
44፥24 ዘፍ1፥1፤ 2፥1፤ኢዮ19፥25፤ መዝ139፥13፤ ኢሳ27፥11፤42፥5፤ 43፥14
44፥25 ዘሌ19፥26፤ 1ሳሙ6፥2፤ ኢዮ5፥13፤መዝ33፥10፤ኢሳ2፥6፤8፥19፤47፥13፤ኤር27፥9፤ ዳን2፥2:10፤4፥7፤ ሚክ3፥7፤ዘካ10፥2፤1ቆሮ1፥19-20:27
44፥26 ዕዝ9፥9፤ መዝ51፥18፤74፥3፤ ኢሳ1፥1፤46፥10፤49፥8-21፤ 51፥3፤55፥11፤59፥21፤61፥4፤ኤር23፥20፤39፥16፤ሰቆ2፥17፤ዳን9፥12፤ ዘካ1፥6፤ማቴ5፥18 44፥27 ኢሳ11፥15፤ 19፥5፤ራእ16፥12

44፥15 *ያመልከዋል ... ወድቆም ይሰግድለታል፤* በቊ17 እና 19 ላይ ተደግሞአል 2፥8:20 ይመ::

44፥16 *ሥጋ ጠብሶበት ... እሳቱን እየሞቀ፤* ዕንጨት ለብዙ አገልግሎት ቢውልም፣ ጣዖት ለመሥራትም ያገለግል ነበር (ቊ19 ይመ)::

44፥17 *አድነኝ፤* በጦርነት ያሸነፈውን የሴይርን መንግሥት አማልክት በማምለኩ ንጉሥ አሜስያስ ተወግዞ ነበር (2ዜና 25፥14-15 ይመ):: ኢሳይያስ እንዲህ ዐይነቱን የጣዖት አምልኮና ምንዝርና ዕውቀት የማጣት ውጤት ነው ይላል (ኢሳ45፥20):: ጣዖት አምላኪዎቹ አምልኮአቸውን ከአማልክት ጋር ቢያያይዙትም፣ ኢሳይያስ አምልኮ ጣዖትን እንደ ከንቱ ነገር፣ እንደ ስንፍና ይቈጥረዋል፤ አማልክት የሉም በማለት አምልኮ ጣዖትን ለ "ግንድ" እንደ መንበርከክ ይቈጥረዋል (ቊ19)

44፥18 *ዐይናቸው ተሸፍኖአል ... ልባቸው ተዘግቶአል፤* በ6፥9-10 የተገለጸው የእስራኤል ሁኔታ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ):: ጣዖታትንና የሚያመልኳቸውን ለማመልከት የቀረበ ሽሙጥ ነው፤ መዝ 82፥5 ይመ::

44፥19 *አስጸያፊ ነገር፤* እግዚአብሔር አምልኮ ጣዖትን ይጸየፋል (ዘዳ 27፥15 ይመ):: በ1ነገ11፥5:7፤ 2ነገ23፥13 ላይ ሞሎክና ካሞሽ አስጸያፊ አማልክት በመባል ይታወቃሉ (41፥24 እና ማብ ይመ):

44፥20 *ዐመድ ይቅማል፤* ራሱን ሙሉ በሙሉ አስገዝቶ ጣዖትን ማምለክም እንኳ ለሚያመልከው የሚያስገኘው አንዳች ጥቅም የለም:: ከሆሴ12፥1 ጋር ያነጻጽሩ:: *ሐሰት፤* ማታለል ማለት ነው፤ 2ተሰ2፥11 ይመ::

44፥21 *ባሪያዬ፤* ቊ1-2፤ 41፥8-9 እና ማብ ይመ::

44፥22 *መተላለፍህን ... አስወግጃለሁ፤* በ40፥2 (የዚያኑ ማብ ይመ) እንደተጠቀሰው፣ የእስራኤል ሥቃይ ይቅርታ እንዲያገኝና ወደ አገሩም እንዲመለስ መንገዱን አመቻችቶለታል (43፥25 እና ማብ ይመ):: *ወደ እኔ ተመለስ፤* ከኤር31፥18 ጋር ያነጻጽሩ:: *ተቤዥቼሃለሁና፤* ከቊ23 ጋር ያነጻጽሩ:: የ35፥9፤ 41፥14፤ 43፥1 ማብ ይመ::

44፥23 *ዘምሩ ... በደስታ ጩኹ፤* ፍጥረት ሁሉ እግዚአብሔርን እንዲያመሰግን የተጠራበት ስፍራ ነው (35፥1፤ 49፥13 ይመ):: *እናንት ተራሮች ... እልል በሉ፤* 49፥13፤ 55፥12 ይመ:: *ክብሩን ገልጦአልና፤* 35፥2 እና ማብ ይመ:: 40፥5 እና ማብ ይመ::

44፥24 *የተቤዠህም፤* 41፥14 እና ማብ ይመ:: *የዘረጋሁ ... ያንጣለልሁ፤* 40፥22 እና ማብ ይመ፤ ከ51፥13 ጋር ያነጻጽሩ::

44፥25 *የሐሰተኞችን ነቢያት ምልክቶች፤* ዘዳ13፥1-3 ይመ:: *ሟርተኞችን፤* የዕብራይስጡ ቃል ከበለዓም (ኢያ13፥22)፣ ከዓይንዶር ሴት ጠንቋይ (1ሳሙ28፥8)፣ ከሐሰተኞች ነቢያት (ኤር27፥9) ጋር አያይዞ ይገልጠዋል:: ምዋርት ከጥንቈላና ከመተት ጋር ግንኙነት አለው (3፥2-3 እና ማብ ይመ፤ ዘዳ18፥10-11 ይመ):: *የጥበበኞችን ... እገለብጣለሁ፤* 29፥14 እና ማብ ይመ::

44፥26 *የባሪያዎቼን ... የመልእክተኞቼን፤* እውነተኛ ነቢያትን ለማለት ነው (42፥19 እና ማብ፤ ኤር7፥25 ይመ):: *መኖሪያ ... ይታነጻሉ፤* ኤር32፥15 ይመ፤ እንዲሁም ከኢሳ58፥12፤ 61፥4 ጋር ያነጻጽሩ:: *ፍርስራሻቸውን አድሳለሁ፤* ከ6፥11 ጋር ያስተያዩ::

44፥27 *ደረቅ ሁን፤* ቀይ ባሕርን ስለ መሻገር የተጠቀሰ ነው

ወንዞችህን አደርቃለሁ' እላለሁ::
[28]ቂሮስንም፣ 'እርሱ እረኛዬ ነው፤
ፈቃዴን ሁሉ ይፈጽማል፤
ኢየሩሳሌምም፣ "እንደ ገና ትሠራ"፣
ቤተ መቅደስም፣ "መሠረቱ ይጣል" ይላል'
እላለሁ::

# 45

"ለቀባሁት፣ ቀኝ እጁን ለያዝሁት፣
ነገሥታትን ትጥቅ አስፈታ ዘንድ፣
ሕዝብን ሁሉ ላስገዛለት፣
ደጆች እንዳይዘጉ፣
በሮቹን በፊቱ ለምከፍትለት፣
ለቂሮስ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
[2]'በፊትህ እሄዳለሁ፤
ተራሮችን[ጣ] እደለድላለሁ፤
የናስ በሮችን እሰብራለሁ፤
የብረት መወርወሪያዎችንም እቈርጣለሁ::
[3]በስምህ የምጠራህ የእስራኤል አምላክ፣
እኔ እግዚአብሔር መሆኔን ታውቅ ዘንድ፣
በተሰወረ ስፍራ የተከማቸውን ሀብት፣
በጨለማም ያለውን ንብረት እሰጥሃለሁ::
[4]ስለ ባሪያዬ ስለ ያዕቆብ፣
ስለ መረጥሁት ስለ እስራኤል፣
አንተ ባታውቀኝ እንኳ፣
በስምህ ጠርቼሃለሁ፤
የክብርም ስም ሰጥቼሃለሁ::
[5]እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤ ከእኔ ሌላ ማንም የለም፤
ከእኔ በቀር አምላክ የለም::
አንተ ባታውቀኝም እንኳ፣
እኔ አበረታሃለሁ::
[6]ይኸውም ሰዎች ከፀሓይ መውጫ፣
እስከ መጥለቂያው፣
ከእኔ በቀር ሌላ እንደሌለ እንዲያውቁ ነው፤
እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤ ከእኔ ሌላ ማንም
የለም::
[7]እኔ ብርሃንን ሠራሁ፤ ጨለማንም ፈጠርሁ፤
አበለጽጋለሁ፤ አደኸያለሁ፤
ይህን ሁሉ የማደርግ እኔ እግዚአብሔር ነኝ::'
[8]"እናንተ ሰማያት፣ ጽድቅን ከላይ አዝንቡ፤
ደመናትም ወደ ታች አንጠብጥቡ፤
ምድር ትከፈት፤
ድነት ይብቀል፤
ጽድቅም አብሮት ይደግ፤
እኔ እግዚአብሔር ፈጥሬዋለሁ::
[9]"ከዐፈር ሸክላዎች መካከል፣
ከሠሪው ጋር ክርክር ለሚገጥም ወዮለት፤
ጭቃ፣ ሸክላ ሠሪውን፣
'ምን እየሠራህ ነው?' ይለዋልን?
የምትሠራውስ ሥራ፣
'እጅ የለህም' ይልሃልን?
[10]አባቱን፣
'የወለድኸው ምንድን ነው?' ለሚል፣
እናቱንም፣
'ምን ወለድሽ'? ለሚል ወዮለት::
[11]"የእስራኤል ቅዱስ፣ ሠሪውም የሆነ እግዚ
አብሔር፣
ስለሚመጡ ነገሮች እንዲህ ይላል፤
'ስለ ልጆቼ ትጠይቁኛላችሁን?
ስለ እጆቼስ ሥራ ታዙኛላችሁን?
[12]ምድርን የሠራሁ እኔ ነኝ፤
ሰውንም በላይዋ ፈጥሬአለሁ፤
እጆቼ ሰማያትን ዘርግተዋል፤
የሰማይንም ሰራዊት አሰማርቻለሁ::
[13]ቂሮስን[ጨ] በጽድቅ አስነሣቸለሁ፤
መንገዱን ሁሉ አስተካክዬለታለሁ፤

2ሳሙ15፥31፤
44፥28 2ዜና36፥22፤ ዕዝ1፥2-4፤ኢሳ14፥32፤ 28፥16፤41፥2፤58፥12
45፥1 2ዜና36፥22፤ መዝ45፥7፤73፥23፤ ኢሳ41፥2፡13፤42፥6፤ 48፥14፤ኤር50፥35፤ 51፥20፡24፤ሚክ4፥13
45፥2 ዘፀ23፥20፤ መዝ107፥16፤147፥13፤ ኢሳ13፥2፤40፥4፤ ኤር51፥30፤ሰቆ2፥9፤ ናሆ3፥13
45፥3 ዘፀ33፥12፤ 2ነገ24፥13፤ኢሳ41፥23፤ 43፥1፤ኤር41፥8፤ 50፥37፤51፥13
45፥4 ኢሳ14፥1፤ 41፥8-9፤ሐሥ17፥23
45፥5 ዘዳ32፥12፤ መዝ18፥31፡39፤ ኢሳ43፥10፤44፥8፤ ሕዝ30፥24-25
45፥6 ቍ5፡18፤ መዝ113፥3፤ ኢሳ11፥9፤14፥13-14፤ 43፥5፤47፥8፡10፤ ሶፎ2፥15
45፥7 ዘፍ1፥4፤ ዘፀ10፥22፤ኢሳ14፥15፤ 31፥2፤ሰቆ3፥38
45፥8 ቍ24፤ መዝ72፥6፤85፥9፡11፤ 133፥3፤ኢሳ12፥3፤ 41፥2፤46፥13፤48፥18፤ 60፥21፤61፥10፡11፤ 62፥1፤ሆሴ10፥12፤ ኢዩ2፥23፤3፥18፤ አሞ5፥24፤ሚል4፥2
45፥9 ኢዮ9፥12፤ 12፥13፤15፥25፤27፥2፤ 33፥13፤መዝ22፥15፤ ኢሳ10፥15፤29፥16፤ ዳን4፥35፤ሮሜ9፥20-21፤1ቆሮ10፥22
45፥11 መዝ8፥6፤ 149፥2፤ኢሳ1፥4፤ 19፥25፤51፥13

2፥1፤ነህ9፥6፤ኢዮ38፥32፤ኢሳ48፥13 45፥13 1ነገ8፥36፤2ዜና36፥22፤ ዕዝ1፥2፤ መዝ26፥12፤ኢሳ40፥4፤ 41፥2፤52፥3

[ጣ]2 የሙት ባሕር ጥቅሎችና የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ከዚህ ጋር ይስማማል፤ በማሶሬቱ ቅጅ ግን የቃሉ ትርጕም አይታወቅም::
[ጨ]13 ዕብራይስጡ፣ እርሱን ይላል::

(11፥15፤ 37፥25፤ 43፥16-17 እና ማብ ይመ፤ ከ50፥2፤ 51፥10 ጋር ያነጻጽሩ)::

44፥28 *ቂሮስንም፤* 41፥2 እና ማብ ይመ:: *እረኛዬ፤* አብዛኛውን ጊዜ ገዦችን የሚያመለክት ነው (2ሳሙ5፥2፤ኤር23፥2 ይመ):: *ኢየሩሳሌምም ... ቤተ መቅደሱም፤* ቤተ መቅደሱ እንደ ገና እንዲሠራ የፈቀደው የቂሮስ ዐዋጅ (ዕዝ1፥2-4፤ 6፥3-5)፣ ኢየሩ ሳሌም ተመልሳ እንድትሠራ ምክንያት ሆኖአል (45፥13 ይመ)::

45፥1 *ለቀባሁት፤* ይህ ቃል፣ "መሲሕ" የሚለውን የዕብራ ይስጥ ቃል ይተካል:: የሌላ አገር ንጉሥ የነበረው ቂሮስ፣ "እረኛዬ" (44፥28) እንደ ተባለ ሁሉ፣ በዚህ ስፍራም፣ "የቀባሁት" ተብሎ ተጠርቶአል:: ይህም እግዚአብሔር መለኮታዊ ፈቃዱን እንዲፈጽምለት ንጉሥ አድርጎ ስለ ሾመው ነው:: እግዚአብሔር፣ ናቡከደነፆርንም እንደዚሁ፣ "አገልጋዬ" ብሎ ጠርቶታል (ኤር25፥9፤ 27፥6፤ 43፥10 ይመ):: አገልጋይ የተባለው ክርስቶስም (የ42፥1-4 ማብ ይመ) በዳን 9፥25-26 ላይ፣ "የተቀባው" ተብሎ ተጠ ርቶአል:: "የተቀባ" የሚለው ቃል በዕብራይስጥ፣ "መሲሕ" ማለት ሲሆን፣ በግሪክ ቋንቋ ደግሞ፣ "ክርስቶስ" ማለት ነው፤ ማቴ1፥17 ይመ)፤ መዝ2፥2 እና ማብ ይመ:: *ቀኝ እጁን ለያዝሁት፤* 41፥13 እና ማብ ይመ::

45፥2 *የናስ በሮችን...የብረት መወርወሪያዎችንም፤* ብዙውን ጊዜ በሮች ከዕንጨት ሲሠሩ መቀርቀሪያዎቹ ብረቶች ነበሩ (መሳ16፥3 እና ማብ ይመ)::

45፥3 *በስምህ የምጠራህ፤* አባባሉ እግዚአብሔር የቂሮስን ድርጊ ት እንደሚቈጣጠረው ያመለክታል፤ ቍ4 ይመ የ43፥1 ማብ ይመ:: *ታውቅ ዘንድ፤* እግዚአብሔር አንድ ነገር ሲያደርግ ኀይሉን ይገልጣል (ከሕዝ 6፥7፤7፥27 ጋር ያነጻጽሩ)::

45፥4 *ባሪያዬ፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ:: *ባታውቀኝ እንኳ፤* ቍ5 ይመ፤ ቂሮስ ባስቀረጸው የድንጋይ ሐውልት ላይ ያመሰገነው የነበረውን ማርዱክ የተባለውን ዋናውን የባቢሎናውያን አምላክ፣ ሳያመልከው አልቀረም:: *የክብርም ስም፤* "የተቀባ" የሚለውን ስም የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ቍ1)::

45፥5 *እኔ ... ከእኔ ሌላ ማንም የለም፤* ቍ6፡14፡18፡21-22፤ 43፥11 እና ማብ ይመ::

45፥6 *መውጫ እስከ መጥለቂያው፤* ምድርን በሙሉ ለማለት ነው (ሚል1፥11 እና ማብ ይመ)::

45፥7 *ጨለማንም ... አደኸያለሁ፤* በግብፃውያን ላይ እንደ ወረደው የመቅሠፍት ጨለማ ዐይነት ሊሆን ይችላል (ዘፀ10፥21-23፤ መዝ105፥28 ይመ፤ ከኢሳ47፥11፤ አሞ3፥6 ጋር ያነጻጽሩ)::

45፥8 *አዝንቡ ... አንጠብጥቡ፤* የተትረፈረፈ በረከት ምሳሌ ነው (ሆሴ10፥12 ይመ):: *ጽድቅ፤* በቍ13፤ 41፥2 ላይ ቂሮስ ከእግዚአብሔር ጽድቅ ጋር ተያይዞ ተገልጦአል:: ይህም እግዚአብሔር በፋርስ ንጉሥ በኩል ትክክለኛውን ነገር ይፈጽማል ማለት ነው:: *ድነት ይብቀል፤* እግዚአብሔር ሕዝቡን ይታደጋል ማለት ነው:: *ጽድቅም አብሮት ይደግ፤* ሰላምና ፍትሕ ይገለጣል (11፥4 እና ማብ ይመ)::

45፥9 *ሸክላ ሠሪው፤* 29፥16 እና ማብ ይመ:: ከ64፥8፤ ከኤር18፥6 ጋር ያነጻጽሩ::

45፥11 *የእስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4 እና ማብ ይመ:: *ስለ ልጆቼ... ስለ እጆቼስ ሥራ፤* 29፥23 እና ማብ ይመ::

45፥12 *ሰማያትን ዘርግተዋል፤* 40፥22 እና ማብ ይመ:: *የሰማይንም ሰራዊት አሰማርቻለሁ፤* 40፥26 እና ማብ ይመ::

45፥13 *ቂሮስን በጽድቅ፤* የ41፥2 ማብ ይመ:: *መንገዱን ሁሉ አስተካክዬለታለሁ፤* ዐላማውን እንዲፈጽም ሁኔታዎችን

ከተማዬን እንደ ገና ይሠራታል፤
ምርኮኞቼን ያለ ክፍያ ወይም ያለ ዋጋ፣
ነጻ ያወጣል፣'
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር።"

[14]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"የግብፅ ሀብትና የኢትዮጵያ ንግድ፣
ቁመተ ረጃጅሞቹ የሳባ ሰዎች፣
ወደ አንተ ይመጣሉ፤
የአንተ ይሆናሉ፤
ከኋላ ይከተሉሃል፤
በሰንሰለትም ታስረው ወደ አንተ በመምጣት፣
በፊትህ እየሰገዱ፣
'በእውነት እግዚአብሔር ከአንተ ጋር ነው፤
ከእርሱም በቀር ሌላ አምላክ የለም'
ብለው ይለምኑሃል።"

[15]አዳኝ የእስራኤል አምላክ ሆይ፤
አንተ በእውነት ራስህን የምትሰውር
አምላክ ነህ።
[16]ጣዖት ሠሪዎች ሁሉ ያፍራሉ፤ ይቀላሉ፤
በአንድነት ይዋረዳሉ።
[17]እስራኤል ግን በእግዚአብሔር፣
በዘላለም ድነት ይድናል፤
እናንተም ለዘላለም፣
አታፍሩም፤ አትዋረዱም።

[18]ሰማያትን የፈጠረ፣
እርሱ እግዚአብሔር ነው፤
ምድርን ያበጃት፣ የሠራት፣
የመሠረታት፣
የሰው መኖሪያ እንጂ፣
ባዶ እንድትሆን ያልፈጠራት፣
እግዚአብሔር እንዲህ ይላልና፤
'እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤
ከእኔም በቀር ሌላ የለም።
[19]በጨለማ ምድር፣
በምስጢር አልተናገርሁም፤
ለያዕቆብም ዘር፣
"በከንቱ ፈልጉኝ" አላልሁም።
እኔ እግዚአብሔር እውነትን እናገራለሁ፤
ትክክለኛውንም ነገር ዐውጃለሁ።'

[20]"በአንድነት ተሰብሰቡ፤ ቅረቡም፤
እናንተ ከአሕዛብ የኰበለላችሁ፣ ኑ።
የዕንጨት ጣዖት የሚሸከሙ፣
ማዳን ወደማይችል አምላክ የሚጸልዩ፣
ዕውቀት የላቸውም።
[21]ጉዳያችሁን ተናገሩ፤ አቅርቡ፤
ተሰብስበውም ይማከሩ።
ይህን አስቀድሞ ማን ዐወጀ?
ከጥንትስ ማን ተናገረ?
እኔ እግዚአብሔር አይደለሁምን?
ጻድቅና አዳኝ የሆነ አምላክ፣
ከእኔ በቀር ማንም የለም፤
ከእኔ ሌላ አምላክ የለም።

[22]"እናንተ የምድር ዳርቻ ሁሉ፣
እኔ አምላክ ነኝ፤ ከእኔም በቀር ሌላ የለምና፤
ትድኑ ዘንድ ወደ እኔ ተመለሱ።
[23]ጕልበት ሁሉ በእኔ ፊት ይንበረከካል፤
አንደበትም ሁሉ በእኔ ይምላል፤
ብዬ በራሴ ምያለሁ፤
የማይታጠፍ ቃል፣
ከአፌ በጽድቅ ወጥቶአል።
[24]ስለ እኔም ሲናገሩ፣ 'ጽድቅና ኀይል፣
በእግዚአብሔር ብቻ ነው' ይላሉ።"
በእርሱ ላይ በቍጣ የተነሡ ሁሉ፣
ወደ እርሱ መጥተው ያፍራሉ።
[25]ነገር ግን የእስራኤል ዘር ሁሉ፣
በእግዚአብሔር ይጸድቃሉ፤ ሞገስንም
ያገኛሉ።

## የባቢሎን አማልክት

**46** ቤል ተዋረደ፤ ናባው እጅግ ዝቅ አለ፤
ጣዖቶቻቸው በአጋሰስ ተጭነዋል[1]፤

45፥12 ዘፍ1፥1፤
45፥14 ዘፍ27፥29፤ 2ሳሙ3፥34፤8፥2፤ መዝ18፥31፤ኢሳ2፥3፤ 11፥9፤14፥1-2፤18፥7፤ 43፥10፤60፥5፡11፤ 62፥2፤ኤር16፥19፤ ዘካ8፥20-23፤ 1ቆሮ14፥25
45፥15 ዘዳ31፥17፤ መዝ44፥24፤ኢሳ1፥15፤ 25፥9
45፥16 መዝ35፥4፤ ኢሳ1፥29
45፥17 ዘፍ30፥23፤ ኢሳ12፥2፤29፥22፤ 41፥11፤ኤር23፥6፤ 33፥16፤ሮሜ11፥26
45፥18 ቍ5፤ ዘፍ1፥1፡2፡26፤ዘዳ4፥35
45፥19 ቍ25፤ ዘዳ4፥29፤30፥11፤ 2ዜና15፥2፤ኢሳ41፥8፤ 48፥16፤65፥4፡9፤ ኤር2፥31፤31፥36
45፥20 ዘዳ32፥37፤ መዝ115፥7፤ኢሳ43፥9፤ 44፥17፡19፤46፥1፤ ኤር1፥16፤2፥28፤ 10፥5
45፥21 ቍ5፤ መዝ3፥8፤11፥7፤ 46፥10፤ኢሳ25፥9፤ 41፥22፤46፥9፡10፤ ማር12፥32
45፥22 ዘፍ49፥10፤ ዘኍ21፥8-9፤ 2ዜና20፥12፤ኢሳ11፥9፡ 12፤44፥22፤49፥6፡12፤ ሆሴ13፥4፤ዘካ12፥10
45፥23 ቍ14፤ ዘፍ22፥16፤ዘዳ30፥11፤ መዝ63፥11፤ኢሳ14፥24፤ 19፥18፤55፥11፤ ሮሜ14፥11፤ ፊል2፥10-11፤ዕብ6፥13
45፥24 ቍ8፤ ዘዳ33፥29፤መዝ18፥39፤ ኢሳ40፥26፤41፥11፤ 63፥1፤ኤር33፥16
45፥25 ቍ19፤ ኢሳ4፥3፤24፥23፤

46፥1 ቍ7፤ 1ሳሙ5፥2፤ኢሳ21፥9፤ 45፥20፤ኤር50፥2፤51፥44

[1] ወይም አውሬና አጋሰስ ብቻ ናቸው

አመቻችቼለታለሁ ማለት ነው (ቍ2፡ 40፥3 እና ማብ ይመ፤ ከምሳ 3፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። *ከተማዬን እንደ ገና ይሠራታል፤* የ44፥28 ማብ ይመ። *ያለ ዋጋ፤* እግዚአብሔር እነርሱን አሳልፎ በሰጠ ጊዜ ዋጋ አልተ ቀበለም ነበርና (52፥3 እና ማብ ይመ፤ ከ43፥3 ማብ ጋር ያስተያዩ)።

45፥14 *ሀብትና ... ንግድ፤* 18፥7 እና ማብ ይመ። *የግብፅ ... የኢትዮጵያ ... የሳባ፤* የ18፥1፤43፥3 ማብ ይመ። *ወደ አንተ ይመጣሉ ... እየሰገዱ፤* 68፥31 ይመ። እስራኤል በቀድሞ ጠላቶቿ ላይ ወደ ፊት የሚኖራት የአገዛዝ ሥልጣን በ11፥14፤ 14፥1-2 (የ14፥1 ማብ ይመ) ተጠቅሶአል፤ የ49፥23፤ 54፥3፤60፥11-14 ጭብጥም ይኸው ነበር። *በእውነት እግዚአብሔር ከአንተ ጋር ነው፤* አንድ ቀን አሕዛብ የእስራኤልን አምላክ ያውቃሉ ማለት ነው (ቍ23፡19፥23-25፤ ዘካ 8፥20-23 ይመ)።

45፥15 *አዳኝ፤* ቍ21 እና በ43፥3 ላይ ያለውን ማብ ይመ። *ራስህን የምትሰውር፤* የእግዚአብሔር ዕቅድና አሠራር ሰው የ ማይደርስበት ምስጢር ነው (ከ54፥8፤ 55፥8-9 ጋር ያነጻጽሩ)።

45፥16 *ያፍራሉ፤* 42፥17፤ 44፥9 ይመ።

45፥17 *በዘላለም ድነት፤* በ54፥8 ከተጠቀሰው "በዘላለማዊ ቸርነቴ" ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ። *አታፍሩም፤* 29፥22 እና ማብ ይመ።

45፥18 *የፈጠረ ... ያበጃት፤* 40፥21-22 እና ማብ ይመ። *ባዶ፤* ወይም "ቅርጽ የለሽ" ወይም "አንዳች ያልነበረባት" ማለት ነው (ዘፍ1፥2 እና ማብ ይመ)። *የሰው መኖሪያ፤* በተጠቀሰው ስፍራ አሁን ሰው የለም (6፥11፤ ኤር4፥23-26 ይመ)፤ ምንም ነገር አልነበረባትም፤ ይሁን እንጂ ሰው የሚኖርበት (44፥26፡28)፣ ሥርዐት የሰፈነበትም ይሆናል።

45፥19 *በጨለማ ... በምስጢር፤* ምናልባት ቀጥተኛ ባል ሆነ መንገድ የአስማተኞችንና የሟርተኞችን ድብቅ ሥራ ለመግለጽ የገባ ነው (8፥19፤ 29፥4 ይመ)። *በከንቱ ፈልጉኝ፤* ከኤር29፥13-14 ጋር ያነጻጽሩ።

45፥20 *ማዳን ወደማይችል ... ዕውቀት የላቸውም፤* 44፥17-18 እና ማብ ይመ።

45፥21 *ተናገሩ፤ አቅርቡ፤* 41፥21-22 እና ማብ ይመ። *አስቀድሞ ማን ዐወጀ? ከጥንትስ፤* 41፥26 እና ማብ ይመ።

45፥22 *የምድር ዳርቻ፤* 11፥12 እና ማብ 42፥10 ይመ። *ትድኑ ዘንድ ወደ እኔ ተመለሱ፤* ከ49፥6 እና በ55፥7 ከተጠ ቀሰው ጥሪ ጋር ያነጻጽሩ።

45፥23 *በራሴ ምያለሁ፤* በዕብ6፥13 ተገልጾአል፤ 62፥8 ይመ። *የማይታጠፍ ቃል፤* 55፥10-11 ይመ። *አንደበትም ሁሉ ... ከአፌ፤* ቍ14 እና ማብ ይመ። ከፍ ያለውን የክርስቶስን ሥልጣን ለማሳየት ጳውሎስ በትንቢተ ኢሳይያስ የተገለጸውን ይህን ክፍል በሮሜ 14፥11 እና በፊል2፥10-11 ላይ ገልጾታል።

45፥24 *ኀይል በእግዚአብሔር ብቻ ነው፤* ቍ 5 እና ማብ ይመ። በምዕራፉ የተገለጸው ዋና ሐሳብ በከፍተኛ ደረጃ የተጠቀሰበት ቦታ ነው። *ያፍራሉ፤* በ41፥11 ላይ ከተጠቀሰው ጋር እጅግ ይመሳሰላል።

45፥25 *ሞገስንም ያገኛሉ፤* ይህ ጥቅስ በ41፥16 ላይ በዕብ ራይስጥ፣ "ክብርን ያገኛሉ" በሚል ተተርጕሞአል።

46፥1 *ቤል፤* የባቢሎናውያን ዋና አምላክ የሆነው የመሮዳክ ሌላ ስም ነው። "ቤል" የሚለው ስም "ባአል" ከተባለው የከነዓ ናውያን አምላክ ጋር አንድ ነው፤ ትርጕሙም "ጌታ" ማለት ነው። *ተዋረደ ... እጅግ ዝቅ አለ፤* በኀፍረት ማለት ነው (ቍ2፤ 21፥9

ይዘዋቸው የሚዞሩት ምስሎች ሸክም ናቸው፤
  ለደከሙ እንስሳት ከባድ ጭነት ናቸው።
2እነርሱም በአንድ ላይ ዝቅ ይላሉ፤ ያጐነብሳሉ፤
  ጭነቱን ለማዳን አይችሉም፤
  ራሳቸውም በምርኮ ይወሰዳሉ።

3"እናንት የያዕቆብ ቤት ሆይ፤
  የእስራኤል ቤት ቅሬታ ሁሉ፣
ከተፀነሳችሁበት ጊዜ ጀምሮ የያዝኋችሁ፣
  ከተወለዳችሁበት ጊዜ ጀምሮ የተሸከምኋችሁ
    ስሙኝ።
4እስከ ሽምግልናችሁ፣ እስከ ሽበትም፣
  የምሸከማችሁ እኔ ነኝ፤ እኔው ነኝ።
ሠርቻችኋለሁ፤ እሸከማችኋለሁ፤
  እደግፋችኋለሁ፤ አድናችኋለሁ።

5"ከማን ጋር ታወዳድሩኛላችሁ? ከማንስ ጋር
    እኩል ታደርጉኛላችሁ?
  እንመሳሰልስ ዘንድ ከማን ጋር ታነጻጽሩ
    ኛላችሁ?
6ሰዎች ወርቅ ከከረጢታቸው ይዘረግፋሉ፤
  ብርንም በሚዛን ይመዝናሉ፤
አንጥረኛን ይቀጥራሉ፤ እርሱም አምላክ አድርጎ
    ያበጅላቸዋል።
  እነርሱም ይሰግዱለታል፤ ያመልኩታልም።
7እንሥተው በትከሻቸው ይሸከሙታል፤
  እቦታው ያደርጉታል፤ በዚያም ይቆማል፤
ከዚያም ቦታ አይንቀሳቀስም፤
  ማንም ወደ እርሱ ቢጮኽ አይመልስም፤
  ከጭንቀቱም አያድነውም።

8"እናንት በደለኞች፣ ይህን አስታውሱ፤
    አስቡበትም፤
  በልባችሁም ያዙት።
9የጥንቱን፣ የቀደመውን ነገር አስታውሱ፤
  እኔ አምላክ ነኝ፤ ከእኔም በቀር ሌላ የለም፤
  እኔ አምላክ ነኝ፤ እንደ እኔ ያለ የለም።
10የመጨረሻውን ከመጀመሪያው፣
  ገና የሚመጣውንም ከጥንቱ ተናግሬአለሁ፤
'ዐላማዬ የጸና ነው፤
  ደስ የሚያሰኘኝንም ሁሉ አደርጋለሁ' እላለሁ።
11ከምሥራቅ ነጣቂ አሞራ፣
  ከሩቅ ምድር ዐላማዬን የሚፈጽም ሰው
    እጠራለሁ።
የተናገርሁትን አደርጋለሁ፤
  ያቀድሁትን እፈጽማለሁ።
12እናንት እልከኞች፣
  ከጽድቅም የራቃችሁ ስሙኝ።
13ጽድቄን እያመጣሁ ነው፤
  ሩቅም አይደለም፤
ማዳኔም አይዘገይም።
  ለጽዮን ድነትን፣
  ለእስራኤል ክብሬን እጐናጸፋለሁ።

41፥16፤49፥4
46፥2 መሳ18፥17-18፤ 1ሳሙ5፥21፤ ኤር51፥47
46፥3 ቍ12፤ ዘዳ1፥31፤መዝ22፥10፤ 28፥9፤139፥13፤ ኢሳ1፥9፤44፥2፤ 48፥12፤51፥1
46፥4 ዘዳ32፥39፤ መዝ18፥35፤71፥18፤ 119፥117፤ኢሳ43፥13
46፥5 ዘፀ15፥11፤ ኢዮ41፥10፤ኢሳ40፥18፡ 25፤ኤር49፥19
46፥6 ዘፀ20፥5፤ ኢሳ40፥19፤44፥17፤ ሆሴ13፥2
46፥7 ቍ1፤ 1ሳሙ5፥3፤1ነገ18፥26፤ ኢሳ41፥7፤44፥17፤ 47፥13
46፥8 ኢሳ1፥2፤ 44፥21፤
46፥9 ዘፀ8፥10፤ ዘዳ32፥7፤ኢሳ41፥22፤ 45፥21፤ማር12፥32
46፥10 ምሳ19፥21፤ ኢሳ7፥7፡9፤41፥4፡22፤ 44፥26፤45፥21፤ ሐሥ5፥39፤ኤፌ1፥11
46፥11 ዘፍ41፥25፤ መሳ4፥10፤ዕዝ1፥2፤ ኢሳ8፥8፤25፥1፤ ኤር44፥28
46፥12 ቍ3፤ ዘፀ32፥9፤ መዝ119፥150፤ ኢሳ9፥9፤48፥1፤ ኤር2፥5
46፥13 መዝ74፥2፤ 85፥9፤ኢሳ1፥26፤ 44፥23፤45፥8፤ ኢዩ2፥32፤ሮሜ3፥21
47፥1 ዘዳ28፥56፤ ኢዮ2፥13፤መዝ137፥8፤ ኢሳ21፥9፤23፥12፤ 29፥4፤ኤር50፥42፤ 51፥33፤ዘካ2፥7
47፥2 ዘፍ24፥65፤ ዘፀ11፥5፤መሳ16፥21፤ ኢሳ32፥11፤ማቴ24፥41

የባቢሎን ውድቀት

47 "አንቺ የባቢሎን[1] ድንግል ልጅ ሆይ፤
  ውረጂ፤ በትቢያ ላይ ተቀመጪ፤
 አንቺ የባቢሎናውያን ልጅ ሆይ፤
  ከዙፋንሽ ውረጂ፤ መሬት ላይ ተቀመጪ፤
ከእንግዲህ ውብ ወይም ለግላጋ፣
  ተብለሽ አትጠሪም።
2ወፍጮ ወስደሽ እህል ፍጪ፤
  መሸፋፈኛሽን አውልቂ፤

ቀሚስሽንም ከፍ ከፍ አድርጊ፤ ባትሽን ግለጪ፤
  እየተንገዳገድሽ ወንዙን ተሻገሪ።
3ዕርቃንሽ ይገለጥ፤
  ኀፍረትሽ ይታይ፤
እበቀላለሁ፤
  እኔ ማንንም አልተውም።
4የሚቤዠን የእስራኤል ቅዱስ፣
  ስሙ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ነው።

47፥3 ዘፍ2፥25፤ ኢሳ1፥24፤13፥18-19፤20፥4፤34፥8፤ሕዝ16፥37፤ ናሆ3፥5 47፥4 ኢዮ19፥25፤ኢሳ1፥4፤13፥4፤48፥2፤ኤር50፥34፤ አሞ4፥13

[1] ወይም በዚህና በቍ5 ላይ *ከለዳውያን*

እና ማብ ይመ)። *ናባው፤* የመማርና የመጻፍ አምላክ ሲሆን፣ የማርዱክ ልጅ ነው።

46፥2 *በምርኮ ይወሰዳሉ፤* ጣዖታትም ከሚያመልኩአቸው ሰዎች ጋር ተማርከው ይሄዳሉ ማለት ነው (ኤር48፥7፤ 49፥3፤ ሆሴ10፥5፤ አሞ1፥15 ይመ)።

46፥3 *ቅሬታ፤* የተረፉትን ለማለት ነው (1፥9 እና ማብ ይመ)። *ከተፀነሳችሁበት... ከተወለዳችሁበት ጊዜ ጀምሮ፤* 44፥2 እና ማብ ይመ።

46፥4 *እስከ ሽምግልናችሁ፣ እስከ ሽበትም፤* ከመዝ37፥25 ጋር ያነጻጽሩ። *የምሸከማችሁ ... ሠርቻችኋለሁ ... አድናችኋለሁ፤* በቍ1-2 ለተጠቀሱት ከንቱ ጣዖታት ግን እንዲህ አይደለም፤ 41፥10፡13፤ 43፥1-2 እና ማብ ይመ።

*46፥5-7፤* 40፥18-20 እና ማብ ይመ።

46፥6 *ይሰግዱለታል፤ ያመልኩታልም፤* 44፥15፡17፡19 ይመ።

46፥7 *ይሸከሙታል፤* ቍ1 ይመ። *አያድነውም፤* 44፥17 እና ማብ ይመ።

46፥8 *በደለኞች፤* እስራኤላውያንን ለማለት ነው። 1፥2 እና ማብ ይመ፤ ከ1፥20፡23፡28፤ 30፥1፤57፥4 ጋር ያነጻጽሩ።

46፥9 *የጥንቱን፤* 41፥22 እና ማብ ይመ። *ሌላ የለም፤* 43፥11 እና ማብ ይመ።

46፥10-11 *ዐላማዬ፤* እግዚአብሔር እስራኤልንና ባቢሎንን በተመለከተ ያለውን ሐሳብና ዕቅድ ለማሳየት ነው (8፥9-10፤ 14፥24፤ 18፥14 እና ማብ ይመ)፤ ከመዝ33፥11 ጋር ያነጻጽሩ።

46፥10 *ከመጀመሪያው፤* 41፥26 እና ማብ ይመ።

46፥11 *ከምሥራቅ ነጣቂ አሞራ፤* የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ ነው (41፥2 እና ማብ ይመ)። የነጣቂ አሞራ ፈጣንነትና ኀይለኛነት በዚህ ስፍራ ተጠቅሶአል (8፥8 እና ማብ፤ ኤር49፥22 ይመ፤ ከዳን8፥4 ጋር ያነጻጽሩ)።

46፥12 *እልከኞች፤* ቍ8፤48፥4፤ ሕዝ2፥4 ይመ።

46፥13 *ጽድቄን፤* በዚህ ስፍራ ከድነት ጋር እኩል ሆኖ ቀርቦአል፤ 41፥2 እና ማብ፤ 45፥8 እና ማብ ይመ። *ማዳኔም፤* የ43፥3 ማብ ይመ። *ክብሬን፤* 35፥2 እና ማብ፤ 40፥5 እና ማብ 44፥23፤49፥3 ይመ።

47፥1 *በትቢያ ላይ ተቀመጪ ... መሬት ላይ፤* የሐዘን ምልክት ነው (3፥26 ይመ)። *የባቢሎን ልጅ ሆይ፤* ባቢሎንንና ነዋሪዎቿን የሚያመለክት ሰውኛ አገላለጽ።

47፥2 *ወፍጮ ... ፍጪ፤* እቤት ውስጥ ሴቶች የሚያከናውኑት ሥራ ነው (ዘፀ11፥15 እና ማብ፤ መሳ9፥53 እና ማብ ይመ)። *ተሻገሪ፤* ምናልባት ወደ ምርኮ መሄድን ለማመልከት ይሆናል።

47፥3 *ዕርቃንሽ ይገለጥ፤* ሕዝ16፥36 ይመ። ባቢሎን ከእንግዲህ ንግሥት አትሆንም (ቍ5፤7 ይመ)፤ ዝቅ ብላ ገረድ ወይም ሴተኛ አዳሪ ሆናለች (ቍ8 ይመ)። *እበቀላለሁ፤* 34፥8 እና ማብ ይመ። *ማንንም አልተውም፤* 13፥18-20 ይመ።

47፥4 *የሚቤዠን፤* የ41፥14 ማብ ይመ። *የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 13፥4 ይመ። *የእስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4፤ 41፥14 እና ማብ ይመ።

[5]“አንቺ የባቢሎናውያን ልጅ ሆይ፤
ወደ ጨለማ ግቢ፤ ዝም ብለሽም ተቀመጪ፤
ከእንግዲህ የመንግሥታት እመቤት፣
ተብለሽ አትጠሪም።
[6]ሕዝቤን ተቈጥቼ ነበር፤
ርስቴን አርክሼው ነበር፤
አሳልፌ በእጅሽ ሰጠኋቸው፤
አንቺ ግን አልራራሽላቸውም፤
በዕድሜ በገፉት ላይ እንኳ፣
እጅግ ከባድ ቀንበር ጫንሽባቸው።
[7]አንቺም፣ ‘እስከ መጨረሻው፣
ለዘላለም ንግሥት እሆናለሁ!’ አልሽ፤
ሆኖም እነዚህን ነገሮች አላስተዋልሽም፤
ፍጻሜያቸው ምን እንደሚሆንም አላሰብሽም።

[8]“አሁንም አንቺ ቅምጥል ፍጡር፣
በራስሽ ተማምነሽ የምትቀመጪ፣
በልብሽም፣
‘እኔ ነኝ፣ ከእኔ በቀር ሌላ የለም፤
ከእንግዲህ መበለት አልሆንም፤
የወላድ መካንም አልሆንም’ የምትይ ስሚ!
[9]እነዚህ ሁለት ነገሮች፣
መበለትነትና የወላድ መካንነት፣
አንድ ቀን ድንገት ይመጡብሻል፤
የቱን ያህል አስማት፣
የቱንም ያህል መተት ቢኖርሽ፣
በሙሉ ኀይላቸው ይመጡብሻል።
[10]በክፋትሽ ተማምነሽ፣
‘ማንም አያየኝም’ አልሽ፤
ደግሞም፣ ‘እኔ ነኝ፣ ከእኔ በቀር ሌላ የለም’
ባልሽ ጊዜ፣
ጥበብሽና ዕውቀትሽ አሳሳቱሽ።
[11]ጥፋት ይመጣብሻል፤
ነገር ግን በአስማትሽ እንዴት እንደም
ታርቂው አታውቂም፤
ወጀ ከፍለሽ ለማስወገድ የማትችዪው፣
ጕዳት ይወድቅብሻል፤
ያላሰብሽው አደጋ፣
ድንገት ይደርስብሻል።
[12]በይ እንግዲህ፣ “ከልጅነትሽ ጀምሮ
የደከምሽባቸውን፣
አስማቶችሽን፣
ብዙ መተቶችን ቀጥዪባቸው፤
ምናልባት ይሳካልሽ፤
ምናልባትም ጠላቶችሽን ታሸብሪባቸው
ይሆናል።
[13]የተቀበልሽው ምክር ሁሉ ድካም ብቻ ሆኖ
አስቀርቶሻል፤
እነዚያ ከወር እስከ ወር ከዋክብትን አንጋጠ
በማየት የሚተነብዩ፣
ኮከብ ቈጣሪዎች እስቲ ይምጡ፤
ከሚደርስብሽም ነገር እስቲ ያድኑሽ።
[14]እነሆ፣ እነርሱ ገለባ ናቸው፤
እሳት ይበላቸዋል፤ ከነበልባሉ ወላፈን
የተነሣ፣
ራሳቸውን ማዳን አይችሉም።
ሰው የሚሞቀው ፍም አይኖርም፤
ተቀምጠው የሚሞቁትም እሳት የለም።
[15]ከልጅነት ጀምሮ አብረሻቸው የደከምሽው፣
አብረሽ የተገበያየሻቸው፣
ሊያደርጉ የሚችሉት ይህንኑ ብቻ ነው።
እያንዳንዱ በስሕተቱ ይገፋበታል፤
አንቺን ግን የሚያድን የለም።

## እልከኛዪቱ እስራኤል

48 “የያዕቆብ ቤት ሆይ፤
እናንተ በእስራኤል ስም የተጠራችሁ፣
ከይሁዳ ዘር የተገኛችሁ፣
እናንተ *በእግዚአብሔር* ስም የምትምሉ፣
በእውነት ወይም በጽድቅ ሳይሆን፣
የእስራኤልን አምላክ የምትጠሩ ይህን ስሙ!
[2]እናንት የቅድስቲቱ ከተማ ነዋሪዎች ነን
ብላችሁ ራሳችሁን የምትጠሩ፣
በእስራኤል አምላክ የምትታመኑ፣

47፥5 ቍ7፤ ኢዮ2፥13፤ኢሳ9፥2፤ 13፥10፡19፤21፥9፤ ሰቆ1፥1፤ራእ17፥18፤ 18፥7
47፥6 ዘዳ13፥15፤ 2ዜና28፥9፤ኢሳ10፥13፤ 14፥6፤42፥24፤ ኤር2፥7፤50፥11
47፥7 ቍ5፤ ዘዳ32፥29፤ኢሳ10፥13፤ 42፥23፡25፤ዳን4፥30፤ ራእ18፥7
47፥8 ኢሳ32፥9፤ 45፥6፤49፥21፤54፥4፤ ሰቆ1፥1፤ራእ18፥7
47፥9 ቍ12፤ ዘዳ18፥10-11፤ መዝ55፥15፤73፥19፤ ኢሳ4፥1፤13፥18፤ ኤር15፥8፤18፥21፤ ናሆ3፥4፤ሚል3፥5፤ 1ተሰ5፥3፤ራእ9፥21፤ 18፥8-10፡23
47፥10 2ነገ21፥16፤ ኢዮ15፥31፤መዝ52፥7፤ 62፥10፤ኢሳ5፥21፤ 29፥15፤44፥20
47፥11 መዝ55፥15፤ ኢሳ10፥3፤14፥15፤ 17፥14፤21፥9፤31፥2፤ ሉቃ17፥27፤1ተሰ5፥3
47፥12 ቍ9፤ ዘፀ7፥11
47፥13 ቍ15፤ ኢሳ5፥29፤19፥3፤ 43፥13፤44፥25፤46፥7፤ 57፥10፤ኤር51፥58፤ ዕን2፥13
47፥14 ኢሳ5፥24፤ 10፥17፤30፥30፤ኤር5 1፥30፡32፡58
47፥15 ቍ13፤ ኢሳ44፥17፤ራእ18፥11
48፥1 ዘፍ17፥5፤ 29፥35፤ዘፀ23፥13፤ 1ሳሙ20፥42፤ 2ሳሙ14፥11፤ መዝ50፥16፤ ኢሳ19፥18፤43፥7፤ 58፥2፤59፥14፤ ኤር4፥2፤5፥2፤7፥9- 10፤44፥26፤ዳን8፥12፤ ዘካ8፥3 48፥2 ነህ11፥1፤ኢሳ1፥26፤10፥20፤47፥4፤ማቴ4፥5፤ ሮሜ2፥17

47፥5 ***የመንግሥታት እመቤት፤*** ባቢሎን እጅግ ውብ ከተማ ነበረች (13፥19 እና ማብ ይመ)።

47፥6 ***ተቈጥቼ ነበር፤ ርስቴን አርክሼው ነበር፤*** 10፥5-6 (አሦር የእግዚአብሔር መሣሪያ የተባለችበትን)፣ 42፥24 እና ማብ፤ 43፥28 እና ማብ ሰቆ 2፥2 ይመ። ***በዕድሜ በገፉት ላይ እንኳ፤*** የደረሰባቸው ሥቃይ፣ ሙሴ ለኪዳኑ በማይታዘዙ ላይ ይመጣል ብሎ የተናገረውን የርግማን ቃል እውን ያደርጋል (ዘዳ28፥49-50)።

47፥7 ***ለዘላለም፤*** በዳን4፥30 ናቡከደነፆር በትዕቢት ከተናገረው ቃል ጋር ያነጻጽሩ።

47፥8፡10 ***እኔ ነኝ፣ ከእኔ በቀር ሌላ የለም፤*** እኔ አምላክ ነኝ የማለትን ያህል መንጠራራት ነው (በ43፥11፤ 45፥5-6፡18፡22 ከተጠቀሰው ከጌታ ቃል ጋር ያነጻጽሩ)፤ 14፥12-15 እና ማብ ይመ።

47፥8 ***በራስሽ ተማምነሽ የምትቀመጪ፤*** በ32፥9፡11 ስለተጠቀሱት ቅምጥል የኢየሩሳሌም ሴቶች የተነገረ ተመሳሳይ አባባል ተገልጾአል። ***መበለት፤*** የተፈታችና የተጨነቀች ሴት ናት። ***የወላድ መካንም፤*** ቍ9፤ 13፥16፡18፤14፥22 ይመ።

47፥9፡12 ***አስማት ... መተት፤*** አደጋ እንዳይደርስ ሲባል ራስን ለመከላከልና በጠላት ላይ ጕዳት ለማምጣት የሚጠቀሙባቸው የጥንቈላ ድርጊቶች ናቸው (3፥2-3 እና ማብ ይመ)።

47፥10 ***ማንም አያየኝም፤*** 29፥15 እና ማብ ይመ።

47፥11 ***ወጀ ከፍለሽ፤*** የሚዶንና የፋርስ ኀይሎች ፍላጎት፣ የእስራኤል ሕዝብ እጁን እንዲሰጥ እንጂ ሌላ ነገር አልነበረም (13፥17 ይመ)።

47፥13 ***ከዋክብትን አንጋጠ በማየት የሚተነብዩ፣ ኮከብ ቈጣሪዎች፤*** ምናልባትም ባቢሎን ከማንኛውም መንግሥት ይልቅ በእንደዚህ ዐይነት ሰዎች ሳትጠቀም አልቀረችም (ዳን2፥2፡10 ይመ)።

47፥14 ***ገለባ፤*** እሳት ሲያገኘው ብው ብሎ የሚነድ ለማለት ነው፤ የ1፥31 ማብ ይመ፤ ከሚል4፥1 ጋር ያነጻጽሩ። ***ራሳቸውን ማዳን አይችሉም፤*** ከነያሉ የእስራኤል አዳኝ ጋር ሲነጻጸሩ (43፥3 እና ማብ ይመ)፣ ኮከብ ቈጣሪዎችና አስማተኞች እንደ ጣዖቶች ሁሉ ከንቱ ናቸው (44፥17 እና ማብ ይመ)። ***ሰው የሚሞቀው ፍም አይደለም፤*** ጣዖት አምላኪዎች ጣዖቶቻቸውን ለመሥራት የሚጠቀሙበትን የማገዶ ዕንጨት በሽሙጥ መግለጽ የሚያስችል ሐረግ ነው (44፥15 ይመ)።

***48፥1 በ ... ስም የተጠራችሁ፤*** የእስራኤል ናቸው ማለት ነው (43፥7 እና ማብ ይመ)። ***እስራኤል፤*** ዘፍ32፥28 እና ማብ ይመ። ***ይሁዳ፤*** ዋናው የደቡብ መንግሥት ነገድ ነው፤ ዘፍ49፥8 እና ማብ ይመ። ***በእውነት ... ሳይሆን፤*** በ65፥16 ላይ ከተጠቀሰው መሐላ ጋር ያስተያዩ።

48፥2 ***የቅድስቲቱ ከተማ፤*** ቤተ መቅደሱ ያለባት ኢየሩሳሌም ናት (2፥2-4 እና ማብ 52፥1፤ 56፥7፤ 57፥13፤ 64፥10-11፤ 65፥11 ይመ)፣ 1፥26 እና ማብ 4፥3 እና ማብ፤ ዳን9፥24 ይመ። ***በ ... አምላክ የምትታመኑ፤*** ቢያንስ ቢያንስ እንኳ በሐሳብ ይህን የምታደርጉ

ስሙ፡ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
የሆነው የሚለውን አድምጡ፤
[3]የቀደሙትን ነገሮች ከብዙ ዘመን በፊት
ተናግሬአለሁ፤
ከአፌ ወጥተዋል፤ እንዲታወቁም
አድርጌአለሁ፤
እኔም ድንገት ሠራሁ እነርሱም፤ ተፈጸሙ።
[4]የቱን ያህል እልኸኛ እንደ ነበርህ ዐውቃለሁና፤
የዐንገትህ ጅማት ብረት፣
ግንባርህም ናስ ነበር።
[5]ስለዚህ እነዚህን ነገሮች ገና ድሮ ነገርሁህ፤
ከመፈጸማቸው በፊት አስታወቅሁህ፤
ይህም፣
'ጣዖቶቼ ይህን አደረጉ፤
ከዕንጨት የተቀረጸው ምስልና ከብረት
የተሠራው አምላኬ ይህን ወስኖአል'
እንዳትል ነው።
[6]እነዚህን ነገሮች ሰምተሃል፤ ሁሉንም
ተመልከታቸው፤
ራስህ ትክክለኛነታቸውን አትመሰክርምን?
"ከአሁን ጀምሮ አዳዲስ ነገሮችን፣
የተሰወሩብህን ያላወቅሃቸውን ነገሮች
እነግርሃለሁ።
[7]እነርሱም የተፈጠሩት አሁን እንጂ ጥንት
አይደለም፤
ስለ እነርሱም ከዛሬ በፊት አልሰማህም።
ስለዚህ፣
'አዎን፤ ስለ እነርሱ ዐውቃለሁ' ማለት
አትችልም።
[8]አልሰማህም ወይም አላውቅህም፤
ጆሮህ ከጥንት የተከፈተ አልነበረም፤
አንተ አታላይ እንደ ነበርህ፣
ከልጅነትህ ጀምሮ ዐመፀኛ
መባልህን ዐውቄአለሁና።
[9]ስለ ስሜ ስል ቍጣዬን አዘገያለሁ፤
ስለ ምስጋናዬም ስል ከአንተ እገታዋለሁ፤
ይኸውም እንዳልቈርጥህ ነው።
[10]እነሆ፤ እንደ ብር ባይሆንም አንጥሬሃለሁ፤
በመከራ እቶን ፈትኜሃለሁ።
[11]ስለ ራሴ፣ ስለ ራሴ ስል አደርጋለሁ፤
ራሴን ለውርደት እንዴት አሳልፌ እሰጣለሁ?
ክብሬን ለማንም አልሰጥም።

## እስራኤል ነጻ ሆነች

[12]"ያዕቆብ ሆይ፤
የጠራሁህ እስራኤል ሆይ፤ ስማኝ፤
እኔ እኔው ነኝ፤
ፊተኛው እኔ ነኝ፤ ኋለኛውም እኔ ነኝ።
[13]ምድርን የመሠረተች የእኔው እጅ ናት፤
ሰማያትን የዘረጋችም ቀኝ እጄ ናት፤
በምጠራቸው ጊዜ፣
ሁሉም በአንድነት ይቆማሉ።
[14]"ሁላችሁም በአንድነት ተሰብሰቡ፤
አድምጡም፤
ከጣዖቶች አስቀድሞ እነዚህን የተናገረ
ማን ነው?
የእግዚአብሔር ምርጥ ወዳጅ የሆነ፣
እርሱ በባቢሎን* ላይ ያቀደውን እንዲፈጽም
ያደርገዋል፤
ክንዱም በባቢሎናውያን ላይ ይሆናል።
[15]እኔ፣ እኔው ራሴ ተናግሬአለሁ፤
በእርግጥ እኔ ጠርቼዋለሁ፤
አመጣዋለሁ፤
ሥራውም ይከናወንለታል።
[16]"ወደ እኔ ቅረቡ፤ ይህን ስሙ፤
"ከመጀመሪያ ጀምሮ በስውር አልተናገርሁም፤
ሲፈጸምም እኔ እዚያው ነበርሁ።"
አሁንም ጌታ እግዚአብሔርና መንፈሱ
ልከውኛል።

48፥3 ኢሳ17፥14፤ 30፥13፤40፥21፤ 41፥22፤45፥21
48፥4 ዘፀ32፥9፤ ዘዳ9፥27፤ኢሳ9፥9፤ ሕዝ3፥9፤ሐሥ7፥51
48፥5 ኢሳ40፥21፤ 42፥9፤ኤር44፥15-18
48፥6 ኢሳ41፥22፤ ሮሜ16፥25
48፥7 ዘፀ6፥7፤ ኢሳ45፥21፤65፥18
48፥8 ዘዳ9፥7:24፤ 29፥4፤መዝ58፥3፤ ኢሳ1፥2:3፤41፥24፤ 43፥27፤58፥1፤ ሚል2፥11:14
48፥9 1ሳሙ12፥22፤ ነህ9፥31፤ኢዮ9፥13፤ ኢሳ30፥18፤37፥35
48፥10 ዘፀ1፥13፤ 15፥25፤1ነገ8፥51፤ ኢሳ1፥25፤ዘካ13፥9፤ ሚል3፥3፤1ጴጥ1፥7
48፥11 ዘሌ18፥21፤ ዘዳ32፥27፤1ሳሙ12፥ 22፤ኢሳ37፥35፤ 42፥8፤ኤር14፥7:21፤ ሕዝ20፥9:14:22:44
48፥12 ኢሳ41፥4: 8፤42፥6፤43፥1:13፤ 46፥3፤ራእ1፥17
48፥13 ዘፍ2፥1፤ ዘፀ20፥11፤ኢዮ9፥8፤ ኢሳ34፥16፤40፥22፤ 42፥5፤45፥18፤51፥16፤ 65፥17፤ዕብ1፥10-12
48፥14 ኢሳ21፥9፤ 41፥2:22፤43፥9፤ 45፥1፤46፥10-11፤ ኤር50፥45
48፥15 ዘኍ4፥10፤ ኢሳ44፥4:28-45
48፥16 ኢሳ11፥2፤ 33፥13፤41፥1፤45፥19፤ 50፥5:7:9፤ዘካ2፥9:11

*14 በዚህና በቍ14 ላይ ወይም፣ *ከለዳውያን*

ለማለት ነው (10፥20)፤ ከ31፥1፤ 36፥6:9፤ ሕዝ29፥6-7 ጋር ያስተያዩ። *የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 13፥4 እና ማብ ይመ።

48፥3 *የቀደሙትን ነገሮች፤* 41፥22 እና ማብ ይመ። *ተፈጸሙ፤* 42፥9 ይመ።

48፥4 *እልኸኛ ... ናስ፤* ኤር6፥28 ይመ፤ ከሕዝ3፥7 ጋር ያነጻጽሩ።

48፥5 *ጣዖቶቼ ይህን አደረጉ፤* ኢሳይያስ ስለ አምልኮ ጣዖት የተናገረውን ከባድ ቃል በ44፥17-20 ይመ (የዚያኑ ማብ ይመ)። *ከዕንጨት የተቀረጸው ምስልና ከብረት የተሠራው አምላኬ፤* 44፥12-20 እና ማብ ይመ።

48፥6 *አዳዲስ ነገሮች፤* ለምሳሌ የእስራኤል መመለስ ሊሆን ይችላል (42፥9 እና ማብ ይመ)፤ የመሲሑን ዘመን፣ አዲሱን ሰማይና አዲሱንም ምድር በዚህ መልክ ማየት ይቻላል (ከ65፥17 ጋር ያነጻጽሩ)። *የተሰወሩብህን፤* ከሮሜ 16፥25-26 ጋር ያነጻጽሩ።

48፥7 *የተፈጠሩት አሁን እንጂ፤* አዳዲስ ነገሮች እንደሚፈጸሙ የተነገረው የነቢያት ቃል እውን መሆኑን የሚያመለክት ነው።

48፥8 *አልሰማህም ወይም አላውቅህም፤* 1፥3 ይመ። *ጆሮህ ... የተከፈተ አልነበረም፤* 6፥10 እና ማብ ይመ። *በዐመፀኝነት፤* 1፥2፤ 46፥8 እና ማብ ይመ።

48፥9 *ቍጣዬን አዘገያለሁ፤* ከመዝ78፥38 ጋር ያነጻጽሩ። *ስለ ምስጋናዬም፤* ለእግዚአብሔር የሚገባውን ምስጋና ለማለት ነው።

48፥10 *አንጥሬሃለሁ ... ፈትኜሃለሁ፤* ፍርድን ቀላጭ አድርገው የሚያሳዩ ምሳሌዎች ናቸው (ኤር9፥7፤ ሕዝ22፥18-22 ይመ)። በ1፥25፤ 4፥4 ላይ ስለሚያጠራው እሳት ተጠቅሶአል። *በመከራ እቶን፤* ግብፅ ለእስራኤላውያን፣ "ብረት ማቅለጫ ምድጃ" ነበረች (ዘዳ4፥20፤ 1ነገ8፥51፤ ኤር11፥4)። የኢየሩሳሌም ውድቀትና የባቢሎን ምርኮ ተመሳሳይ ምድጃዎች ናቸው።

48፥11 *ለውርደት፤* የኢየሩሳሌም ውድቀትና የእግዚአብሔር ሕዝብ መበተን ለእግዚአብሔር ስም ኀፍረትን አስከትሉአል (ሕዝ36፥20-23 ይመ)። *ክብሬን፤* 40፥5 እና ማብ ይመ።

48፥12 *የጠራሁህ፤* የተመረጠው ሕዝብ የእግዚአብሔር አገልጋይ እንዲሆን ተጠርቶአል ማለት ነው፤ 42፥6፤ 41፥2፤ 43፥1 እና ማብ ይመ። *ፊተኛው ... ኋለኛውም፤* 41፥4 እና ማብ ይመ።

48፥13 *ምድርን የመሠረተ ... ሰማያትን የዘረጋም፤* ኢሳይያስ ምንጊዜም እግዚአብሔር ፈጣሪ መሆኑን ይናገራል (40፥21-22፤ 42፥5፤ 51፥13 እና ማብ ይመ)፤ ከመዝ102፥25 ጋር ያነጻጽሩ። *በምጠራቸው ጊዜ፣ ሁሉም ... ይቆማሉ፤* ፍጥረታት ሁሉ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ይፈጽማሉ (40፥26 እና ማብ፤ መዝ103፥22 ይመ)።

48፥14 *ከጣዖቶች አስቀድሞ ... የተናገረ፤* 41፥21-23:26፤ 43፥9 እና ማብ ይመ። *ምርጥ ወዳጅ፤* ታላቁን ቂሮስን ነው (41፥2 እና ማብ ይመ)። *ያቀደውን፤* 46፥10-11 እና ማብ ይመ። *በባቢሎን፤* 13፥1 እና ማብ ይመ።

48፥15 *ጠርቼዋለሁ፤* ቂሮስን ለማለት ነው (41፥2 እና ማብ ይመ)። *ይከናወንለታል፤* 44፥28፤ 45፥1-4 እና ማብ ይመ።

48፥16 *ከመጀመሪያ ጀምሮ፤* ስለ ቂሮስና ስለ ተልእኮው የተጠቀሰ ነው (41፥25-27 እና ማብ ይመ)። *በስውር አልተናገርሁም፤* 45፥19 እና ማብ ይመ። *እግዚአብሔርና መንፈሱ ልከውኛል፤* ኢሳይያስን ወይም የእግዚአብሔር አገልጋይ የተባለውን ያመለክታል። የእግዚአብሔር መንፈስ በ42፥1 ላይ በተጻፈው የእግዚአብሔር አገልጋይና (የዚያኑ ማብ ይመ) በ61፥1 ላይ በተጠቀሰው መሲሕ ላይ ወርዶአል (የዚያኑ ማብ ይመ)።

[17]የተቤዠህ፣ የእስራኤል ቅዱስ፣
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"እኔ *እግዚአብሔር* አምላክህ፣
የሚበጅህ ምን እንደ ሆነ የማስተምርህ፣
መሄድ በሚገባህ መንገድ የምመራህ ነኝ::
[18]ትእዛዜን ሰምተህ ብቻ ቢሆን ኖሮ፣
ሰላምህ እንደ ወንዝ፣
ጽድቅህም እንደ ባሕር ሞገድ በሆነ ነበር::
[19]ዘርህ እንደ አሸዋ፣
ልጆችህ ስፍር እንደሌለው ትቢያ በሆኑ
ነበር፤
ስማቸው አይወገድም፤
ከፊቴም አይጠፋም::
[20]ከባቢሎን ውጡ፣
ከባቢሎናውያንም ሽሹ!
ይህን በእልልታ አስታውቁ፤ ዐውጁት፤
እስከ ምድር ዳርቻ ድረስ ተናገሩ፤
"*እግዚአብሔር* ባሪያውን ያዕቆብን
ተቤዥቶታል" በሉ::
[21]በምድረ በዳ ሲመራቸው አልተጠሙም ነበር፤
ውሃ ከዐለት አፈለቀላቸው፤
ዐለቱን ሰነጠቀ፤
ውሃውም በኀይል ፈልቆ ወጣ::
[22]"ለክፉዎች ሰላም የላቸውም" ይላል *እግዚአብሔር*::

## የእግዚአብሔር ባሪያ

**49** እናንተ ደሴቶች ስሙኝ፤
እናንተ በሩቅ ያላችሁ ሕዝቦች
ይህን አድምጡ፤
በእናቴ ማሕፀን ሳለሁ *እግዚአብሔር* ጠራኝ፤
ከመወለዴ በፊት በስም ጠራኝ::
[2]አፌን እንደ ተሳለ ሰይፍ አደረገው፤
በእጁ ጥላ ሰወረኝ፤
የተወለወለ ፍላጻ አደረገኝ፤
በሰገባውም ውስጥ ሸሸገኝ::
[3]እርሱም፣ "እስራኤል፤ አንተ ባሪያዬ ነህ፤
በአንተ ክብሬን እገልጣለሁ" አለኝ::
[4]እኔ ግን፣ "በላሜ ሳይኖረኝ እንዲሁ ደከምሁ፤
ምንም ጥቅም ለሌለውና ለከንቱ ነገር
ጕልበቴን ጨረስሁ፤
ሆኖም ግን ብድራቴ *በእግዚአብሔር* እጅ፣
ዋጋዬም በአምላኬ ዘንድ ነው" አልሁ::
[5]*በእግዚአብሔር* ዐይን ፊት ከብሬአለሁ፤
አምላኬ ጕልበት ሆኖልኛል፤
ባሪያው እንድሆን ከማሕፀን የሠራኝ፣
ያዕቆብን ወደ እርሱ እንድመልስ፣
እስራኤልን ወደ እርሱ እንድሰበስብ ያደረገኝ፣
*እግዚአብሔር* አሁንም እንዲህ ይላል፤
[6]እርሱም፣
"ባሪያዬ መሆንህ፣
የያዕቆብን ነገዶች እንደ ገና መመለስህ፣
የጠበቅኋቸውን እስራኤል መልሰህ
ማምጣት

48፥17 ኢዮ19፥25፤ ኢሳ28፥9፤30፥11፤ 47፥4፤49፥7፡10፤ 54፥8፤57፥18፤58፥11፤ ኤር7፥13
48፥18 መዝ147፥14፤ ኢሳ1፥26፤9፥7፤33፥21፤ 42፥23፤45፥8፤54፥13፤ 66፥12
48፥19 ዘፍ12፥2፤ ኢዮ5፥25፤ኢሳ43፥5፤ 44፥3፤56፥5፤61፥9፤ 65፥23፤66፥22፤ ኤር35፥19
48፥20 ዘፍ49፥10፤ ዘፀ6፥6፤ዘዳ30፥4፤ ኢሳ12፥6፤33፥24፤ 49፥13፤51፥11፤ 52፥9፡11፤63፥9፤ ኤር25፥22፤48፥6፤ 50፥8፤ 51፥6፡45፤ ሚክ4፥10፤ዘካ2፥6-7፤ ራእ18፥4
48፥21 ዘኍ20፥11፤ ኢሳ30፥25፤33፥16፤ 35፥6
48፥22 ኢዮ3፥26፤ ኢሳ3፥11፤57፥21
49፥1 ዘፀ33፥12፤ ኢሳ7፥14፤9፥6፤11፥11፤ 33፥13፤43፥1፤44፥2፡ 24፤46፥3፤ኤር1፥5፤ ማቴ1፥20፤ገላ1፥15
49፥2 ዘፀ33፥22፤ ዘዳ32፥23፤ኢዮ40፥18፤ መዝ64፥3፤91፥1፤ ዘካ9፥13፤ኤፌ6፥17፤ ራእ1፥16
49፥3 ዘሌ10፥3፤ ኢሳ20፥3፤44፥23፤ ዘካ3፥8
49፥4 ዘሌ26፥20፤ኢዮ27፥2፤ኢሳ35፥4፤45፥25፤50፥8፤53፥10፤54፥17፤ 55፥2፤65፥23 49፥5 ዘዳ30፥4፤መዝ18፥1፤39፥13፤ኢሳ11፥12፤43፥4፤ ገላ1፥15 49፥6 ቍ3፤ ዘዳ30፥4፤መዝ48፥10፤ኢሳ1፥9፤9፥2፤26፥18፤ 55፥5፤ዘካ8፥22፤ማቴ28፥19፤ሉቃ2፥32፤ዮሐ1፥9፤11፥52፤ሐሥ13፥47

48፥17 *የተቤዠህ፣ የእስራኤል ቅዱስ፤* 41፥14 እና ማብ ይመ:: *የማስተምርህ መሄድ በሚገባህ መንገድ፤* በነቢያት አማካይነት ለማለት ነው (30፥20-21 እና ማብ፤ መዝ 32፥8 ይመ)::

48፥18 *ሰላምህ እንደ ወንዝ፣ ጽድቅህም እንደ ባሕር ሞገድ፤* የተትረፈረፈና የሚፈስ ሰላምና ጽድቅ ይሆናል ማለት ነው (45፥8 እና ማብ፤ አሞ5፥24 ማብ ይመ):: ሰላምና ጽድቅ በ9፥7፤ 32፥17፤ 54፥13-14፤ 60፥17፤ መዝ85፥10፤ ዕብ7፥2 ላይም ተያይዘው ተጠቅሰዋል::

48፥19 *ዘርህ እንደ አሸዋ፤* 10፥22፤ ዘፍ13፥16 እና ማብ፤ ዘፍ 22፥17፤ ኤር33፥22 እና ማብ ይመ:: *ስማቸው አይወገድም፤* የእስራኤል ስም ፈጽሞ አይጠፋም (ቍ9፤ 54፥3 ይመ)::

48፥20 *ከባቢሎን ውጡ … ሽሹ፤* እስራኤላውያን መሸሽ ባያስፈልጋቸውም እንኳ (52፥12 ይመ)፣ በባቢሎን ላይ ከሚመጣው ፍርድ ለማምለጥ ፈጥነው እንዲወጡ የተሰጣቸው ማሳሰቢያ ነው (ከራእ18፥4 ጋር ያነጻጽሩ):: ኢሳይያስ የባቢሎንን ስም ለመጨረሻ ጊዜ የጠቀሰው በዚህ ስፍራ ነው:: *በእልልታ፤* 44፥23፤ 49፥13፤ 52፥9 እና ማብ ይመ:: *የምድር ዳርቻ፤* 11፥12፤ 42፥10 እና ማብ ይመ:: *ተቤዥቶታል፤* 43፥1 እና ማብ ይመ:: *ባሪያውን፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ::

*48፥21 አልተጠሙም ነበር፤ ውሃ ከዐለት፤* ሕዝቡ ከምድረ ግብፅ ከወጡ በኋላ እግዚአብሔር በቸርነቱ የሠራውን የሚያመለክት ሐረግ ነው (ዘፀ17፥6 እና ማብ፤ ዘኍ20፥11፤ ኢሳ32፥2፤ 35፥6፤ 43፥19፤ 49፥10 እና ማብ ይመ):: የእግዚአብሔር ሕዝብ ከባቢሎን ምርኮ ወደ አገራቸው ሲመለሱም በመንገድ ላይ ውሃ ይፈልቅላቸዋል::

*48፥22፤* በ57፥21 ላይ ቃል በቃል ተደግሞአል:: *ለክፉዎች፤* በእግዚአብሔር ላይ የሚያምፁ ናቸው (የ1፥2 ማብ ይመ):: *ሰላም፤* 39፥8 እና ማብ ይመ::

*49፥1-6* (ወይም 1-7 ወይም1-13)፤ አገልጋዩ ከሚዘምራቸው አራት መዝሙሮች መካከል ይህ ሁለተኛው ነው (የ42፥1-4 ማብ ይመ)::

49፥1 *ደሴቶች፤* ወይም "ጠረፎች" ማለት ነው:: በ42፥14 ላይ ደሴቶች በአገልጋዩ ሕግ፣ "ተስፋ ያደርጋሉ" ተብሎ ተጽፎአል:: *በእናቴ ማሕፀን ሳለሁ እግዚአብሔር ጠራኝ፤* ከቍ5 ጋር ያነጻጽሩ:: አባባሉ ከነቢዩ ኤርምያስ (ኤር1፥5)፣ ከሐዋርያው ጳውሎስ (ገላ1፥15) መጠራት ጋር ተመሳሳይ ነው፤ ከ41፥9 ጋር ያነጻጽሩ:: *ከመወለዴ በፊት ጠራኝ፤* 43፥1 እና ማብ ይመ::

49፥2 *አፌን እንደ ተሳለ ሰይፍ፤* ኤፌ6፥17፤ ዕብ4፥12፤ ራእ1፥16፤ 2፥12፡16 ይመ:: በ11፥4 ላይ ከመሲሑ አፍ ኀይለኛ በትር እንደሚወጣ ተጠቅሶአል:: *በእጁ ጥላ፤* ጥበቃን የሚገልጽ ሐረግ ነው (30፥2-3፤51፥16 ይመ):: *የተወለወለ ፍላጻ፤* ፍላጾች በዘዳ 32፥23፡42 ላይ የእግዚአብሔርን ፍርድ ለማመልከት ተጠቅሰዋል፤ የክፉዎችን መርዘኛ ቃል (መዝ64፥3-4)፣ የሰይጣን ተንኰልና ፈተናዎች (ኤፌ6፥11፡16) ለማሳየትም ጥቅም ላይ ውለዋል::

49፥3 *እስራኤል አንተ ባሪያዬ ነህ፤* 41፥8-9፤42፥1-4፤42፥1 ማብ ይመ:: በቍ5 ላይ ይህ አገልጋይ ለእስራኤል ልዩ ተልእኮ ስላለው፣ "አገልጋይ" የሚለው ቃል እዚህ ላይ የእስራኤልን ሕዝብ ቃል በቃል የሚያመለክት ሊሆን አይችልም፤ ይልቁንም አገልጋዩ መሲሕ እግዚአብሔር የሚከብርበት እውነተኛው እስራኤል ነው፤ የእስራኤል ምድር ብትወድቅም እርሱ ድል አድራጊ ይሆናል:: *ክብሬን እገልጣለሁ፤* ቤዛ በመሆን ይህን ያከናውናል ማለት ነው (የ35፥2፤40፥5 ማብ ይመ)::

49፥4 *በላሜ ሳይኖረኝ እንዲሁ ደከምሁ… ለከንቱ ነገር፤* የእስራኤል ምድር ለከንቱ ነገር እንደ ደከመች (65፥23 ይመ)፣ ክርስቶስም በአገልግሎቱ ወቅት ብዙ ተቃውሞ እንደሚሰነዘርበትና እንደሚሠቃይ ያመለክታል:: "የሚሠቃየው አገልጋይ" ጭብጥ ከአራቱ የአገልጋይ መዝሙሮች ውስጥ በሦስተኛውና በአራተኛው ላይ ዕድገት አሳይቶአል (50፥4-9 ወይም 50፥4-11፤ 52፥13-53፥12):: *ብድራቴ… ዋጋዬም፤* ምናልባት የአገልጋዩን መንፈሳዊ ዘር (53፥10 ይመ) ማለትም በእርሱ የሚያምኑትን አይሁድና አሕዛብ ለመጥቀስ የተነገረ ነው (ቍ 5-6)፤ 40፥10 እና ማብ ይመ:: እርሱ ከፍ ከፍ ይላል፤ ዋጋውንም ይቀበላል (50፥8፤ 53፥10-12፤ 1ጢሞ 3፥16)::

49፥5 *ጕልበት፤* 12፥2 ይመ:: *ከማሕፀን የሠራኝ፤* ቍ1፤ 44፥2 እና ማብ ይመ:: *ያዕቆብን … እንድመልስ … እስራኤልን … እንድሰበስብ፤* ከባቢሎን ምርኮ ነጻ ስለመውጣትና (ቍ 9-12፡22፤ 41፥2 እና ማብ ይመ) ከታላቁ ኀጢአት ባርነት ምርኮ ነጻ ስለ መውጣት የተነገረ ትንቢት ነው (42፥7 እና ማብ ይመ)::

*49፥6፤* ይህ ጥቅስ አንዳንድ ጊዜ ከዘፍ12፥1-3፤ ዘፀ19፥5-6 ጋር በመደመር፣ "የብሉይ ኪዳን ታላቁ ተልእኮ" ተብሎ ይጠራል:: በሐሥ13፥47 ላይም በጳውሎስና በበርናባስ በከፊል ተጠቅሶአል:: *የጠበቅኋቸውን፤* ምናልባት የተረፉትን ቅሬታዎች ለማመልከት

ለአንተ ቀላል ነገር ነው፤
ድነቴን እስከ ምድር ዳርቻ እንድታመጣ፣
ለአሕዛብ ብርሃን አደርግሃለሁ” አለኝ።

7 *እግዚአብሔር*፣
ታዳጊ የሆነው የእስራኤል ቅዱስ፣
ለተናቀውና በሕዝብ ለተጠላው፣
የገዦች አገልጋይ እንዲህ ይላል፤
“ነገሥታት አይተውህ ይነሣሉ፤
ልዑላንም አይተው፤ ይሰግዳሉ፤
ምክንያቱም የመረጠህ የእስራኤል ቅዱስ፣
*እግዚአብሔር* ታማኝ ነው።”

## የእስራኤል እንደ ገና መቋቋም

8 *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
“በወደድሁ ጊዜ እመልስልሃለሁ፤
በድነትም ቀን እረዳሃለሁ።
ለሕዝቡ ቃል ኪዳን እንድትሆን፣
ምድሪቱን እንደ ገና እንድትሠራት፣
ጠፍ የሆኑትን ርስቶች ለየባለቤታቸው
እንድትመልስ፣
እጠብቅሃለሁ፤ እሠራሃለሁም፤
9 የተማረኩትን፣ ‘ኑ ውጡ’
በጨለማ ያሉትን፣ ‘ነጻ ሁኑ’ እንድትል
አድርጌሃለሁ።
“በየመንገዱ ዳር ይመገባሉ፤
በተራቈተውም ኰረብታ ሁሉ ላይ
መሰማሪያ ያገኛሉ።
10 አይራቡም፤ አይጠሙም፤
የምድረ በዳ ትኵሳት ወይም የፀሓይ ቃጠሎ
አይጐዳቸውም።
የሚራራላቸው ይመራቸዋል፤
በውሃ ምንጭ ዳርም ያሰማራቸዋል።
11 ተራሮቼን ሁሉ መንገድ አደርጋለሁ፤
ጐዳናዎቼም ከፍ ይላሉ።
12 እነሆ፤ ከሩቅ አገር ይመጣሉ፤
አንዳንዶች ከሰሜን ሌሎች ከምዕራብ፣
የቀሩት ደግሞ ከሲኒም[ሥ] ይመጣሉ።

13 ሰማያት ሆይ፤ እልል በሉ፤
ምድር ሆይ፤ ደስ ይበልሽ፤
ተራሮች ሆይ፤ በደስታ ዘምሩ፤
*እግዚአብሔር* ሕዝቡን ያጽናናል፤
ለተቸገሩትም ይራራልና።

14 ጽዮን ግን፣ “*እግዚአብሔር* ትቶኛል፤
ጌታም ረስቶኛል” አለች።

15 “እናት የምታጠባውን ልጇን ልትረሳ
ትችላለችን?
ለወለደችውስ ልጅ አትራራለትምን?
ምናልባት እርሷ ትረሳ ይሆናል፣
እኔ ግን አልረሳሽም።
16 እነሆ፤ በእጄ መዳፍ ላይ ቀርጬሻለሁ፤
ቅጥሮችሽ ምንጊዜም በፊቴ ናቸው።
17 ወንዶች ልጆችሽ ፈጥነው ይመለሳሉ፤
ያፈራረሱሽም ከአንቺ ይሸሻሉ።
18 ዐይንሽን ቀና አድርጊ፤ ዙሪያውንም ተመልከቺ፤
ወንዶች ልጆችሽ ሁሉ ተሰብስበው ወደ
አንቺ ይመጣሉ።
“በሕያውነቴ እምላለሁ፤
እነዚህን ሁሉ እንደ ጌጥ ትለብሻቸዋለሽ፤
እንደ ሙሽራም ትጐናጸፊያቸዋለሽ”
ይላል *እግዚአብሔር*።

49፥7 ዘዳ27፥29፤ ዘጸ7፥9፤ዕዝ1፥2፤ መዝ22፥6፡29፤ 69፥7-9፤86፥9፤ ኢሳ14፥1፤48፥17፤ 52፥15፤1ቆሮ1፥9
49፥8 ዘሌ25፥10፤ ዘኍ34፥13፤ መዝ37፥9፤69፥13፤ ኢሳ5፥2፤26፥3፤ 41፥10፤42፥6፤44፥26፤ 58፥12፤60፥10፡21፤ 61፥2፡4፤ሕዝ36፥10፡ 33፤አሞ9፥11፡14፤ 2ቆሮ6፥2
49፥9 መዝ107፥10፤ ኢሳ41፥18፤42፥7፤ 61፥1፤ሉቃ4፥19
49፥10 መዝ48፥14፤ 121፥6፤ኢሳ14፥1፤ 33፥16፡21፤35፥7፤ 42፥16፤48፥17፤ ራእ7፥16
49፥11 ኢሳ11፥16፤ 40፥4፤ኤር31፥9
49፥12 ኢሳ2፥3፤ 11፥11፤43፥5-6፤ 59፥19፤ማቴ8፥11
49፥13 መዝ9፥12፤ 65፥12-13፤71፥21፤ 96፥11፤98፥4፤ ኢሳ14፥1፤40፥1፤ 44፥23፤48፥20፤ 2ቆሮ1፥4
49፥14 መዝ9፥10፤ 71፥11፤ኢሳ27፥8፤ 40፥9
49፥15 1ነገ3፥26፤ ኢሳ44፥21፤66፥13
49፥16 ዘፍ38፥18፤ ዘፀ28፥9፤መዝ48፥12-13፤ኢሳ62፥6
49፥17 ኢሳ5፥6፤ 10፥6፤37፥18
49፥18 ዘኍ14፥21፤ኢሳ11፥12፤14፥1፤ 43፥5፤45፥23፤51፥3፤52፥1፤ 54፥7፡9፤61፥10፤62፥8፤ኤር2፥32፤ ሮሜ14፥11

[ሥ]12 የማሶሬቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማል፣ የሙት ባሕር ጥቅሎች ግን፣ *አስዋን* ይላሉ።

ይሆናል (1፥9 እና ማብ ይመ)። *እስከ ምድር ዳርቻ፤* 11፥12 እና ማብ 41፥5፤ 42፥10፤ 48፤20 ይመ።*ለአሕዛብ ብርሃን፤* 42፥6 እና ማብ፤ ሐሥ26፥23 ይመ። ክርስቶስ የዓለም ብርሃን ነው (ሉቃ2፥30-32፤ ዮሐ8፥12፤ 9፥5)፤ ክርስቲያኖችም የእርሱን ብርሃን ያንጸባርቃሉ (ማቴ5፥14)።

49፥7 *ታዳጊ የሆነው የእስራኤል ቅዱስ፤* 41፥14 እና ማብ ይመ። *ለተናቀውና፤* ይህ አባባል ስለሚሠቃየው አገልጋይ በ53፥3 ላይ ሁለት ጊዜ ተጠቅሶአል። በ60፥14 ላይ ጽዮን በጠላቶቿ ተንቃለች። *በሕዝብ፤* ይህ አባባል እስራኤልን (1፥4) ወይም ደግሞ አሕዛብን ሊያመለክት ይችላል። *ነገሥታት አይተውህ ... ይሰግዳሉ፤* ቍ23 ይመ። ለአገልጋዩ የሚደረገው ይህ ሁኔታ በ52፥15 ላይ ከተገለጸው ጋር ተመሳሳይ ነው። ቀደም ሲል ጨቋኞች የነበሩ በ60፥14 ላይ እንደ ተገለጸው ኢየሩሳሌም እንደ ገና በምትሠራበት ጊዜ ይሰግዱለታል (ከ45፥14፤60፥11-12፤ 66፥28 ጋር ያነጻጽሩ)። *የመረጠህ፤* 41፥8-9፤ 42፥1 እና ማብ ይመ።

*49፥8፤* በ2ቆሮ6፥2 ላይ በከፊል ተጠቅሶአል። *በወደድሁ ጊዜ ... በድነትም ቀን፤* የዚህ ጥቅስ መነሻ ምናልባት የኢዮቤልዩ ዓመት ሊሆን ይችላል (61፥1-2፤ ዘሌ25፥10 ይመ)። በዚያ በነጻነቱ ዓመት እንደ ሆነው ሁሉ ከምርኮ መመለሱ ምድሪቱን ተመልሳ በሕዝቡ እጅ እንድትገባ ያደርጋታል። *ኪዳን እንድትሆን ... እጠብቅሃለሁ፤* 42፥6 እና ማብ ይመ። *ጠፍ የሆኑትን ርስቶች ... እንድትመልስ፤* 44፥26 ይመ። ምድሪቱ በእያንዳንዱ ነገድና ቤተ ሰብ መካከል ተከፋፍላ የተሰጠችው በኢያሱ ነበር (ኢሱ14፥1-5)። መሲሑ አገልጋይ አዲሱን ኢያሱ ብቻ ሳይሆን፣ አዲሱን ሙሴም ይሆናል (ቍ9-10 ይመ፤ ይህም እስራኤላውያን ከግብፅ ባርነት ነጻ የወጡበትንና ከዚያም በሙሴ መሪነት በምድረ በዳ ያሳለፏቸው የመከራ ዓመታት ያስተጋባል)።

49፥9 *የተማረኩትን፤* በምርኮ ተገደው የሄዱትን ለማለት ነው፤ 42፥7 እና ማብ ይመ። *በተራቈተውም ኰረብታ፤* 41፥18 እና ማብ ይመ።

49፥10 *አይራቡም፤ አይጠሙም፤* 48፥21 እና ማብ ይመ። *የሚራራላቸው፤* 14፥1 እና ማብ ይመ። *ይመራቸዋል፤* እንዳገራቸው እረኛ ፊት ፊታቸው እየሄደ ማለት ነው (40፥11 እና ማብ ይመ)። እንደ ራእ7፥16-17 ጠቅላላ ጥቅሱ መንግሥተ ሰማያትን ያሳያል።

49፥11 *ተራሮቼን ሁሉ መንገድ፤* 26፥7 እና ማብ ይመ። *ጐዳናዎቼም ከፍ ይላሉ፤* 11፥16፤ 35፥8፤ 40፥3፤ 62፥10 እና ማብ ይመ።

49፥12 *ከሩቅ አገር ይመጣሉ፤* 11፥11 እና ማብ 60፥4 ይመ። *ከሰሜን ሌሎች ከምዕራብ፤* 43፥5-6 እና ማብ ይመ። *ከሲኒም፤* ሕዝ 29፥10፤ 30፥6 ይመ። ከግብፅ በስተ ደቡብ ጫፍ ላይ የሚገኝ ስፍራ ነው።

49፥13 *እልል በሉ፤ ... ተራሮች ሆይ፤* በኢሳይያስ መጽሐፍ ተፈጥሮ ብዙ ጊዜ እንደ ሰው ተገልጦአል 44፥23 እና ማብ ይመ። *ሕዝቡን ያጽናናል፤* ሲያድናቸውና ሲታደጋቸው ማለት ነው። ከ2ቆሮ1፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ። *ይራራልና፤* ቍ10 እና ማብ ይመ፤ 54፥7-10 ይመ።

49፥14 *ትቶኛል ... ረስቶኛል፤* 40፥27፤ 54፥7፤ ሰቆ5፥20-22 ይመ።

49፥15 *እናት ... ልትረሳ ትችላለችን?* ከመዝ27፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

49፥16 *በእጄ ... ቀርጬሻለሁ፤* በእግዚአብሔር ፊት መታሰቢያ እንዲሆኑ የእስራኤል ነገዶች ስም ሁሉ በድንጋይ ተቀርጾ በሊቀ ካህናቱ ኤፉድ ላይ እንደሚንጠለጠል ማለት ነው (ዘፀ28፥9-12 ይመ፤ ከማሕ 8፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። *ምንጊዜም በፊቴ፤* ከመዝ137፥5-6 ጋር ያነጻጽሩ።

49፥17 *ወንዶች ልጆችሽ፤* በሙት ባሕር ጥቅል ብራናና በአንዳንድ የጥንት ቅጆችን ሐሳብ መሠረት፣ “ገንቢዎች” ማለት ነው (የ62፥5 ማብ ይመ)።

49፥18 *ወንዶች ልጆችሽ ሁሉ ተሰብስበው፤* ቍ5፡12 እና ማብ ይመ። *እንደ ጌጥ፤* ውብ የሆኑ ልብሶችና ጌጣ ጌጦች ኀይልንና ደስታን በምሳሌነት ያሳያሉ።

[19]“ፈራርሰሽ ባድማ ብትሆኚ፣
ምድርሽ ፈጽሞ ቢጠፋ፣
ዛሬ ለሕዝብሽ ጠባብ ብትሆኚም እንኳ፣
የዋጡሽ ከአንቺ ይርቃሉ።
[20]በሐዘንሽ ዘመን የወለድሻቸው ልጆች፣
ጆሮሽ እየሰማ፣
‘ይህ ቦታ በጣም ጠበናል፤
የምንኖርበት በቂ ስፍራ ስጪን’ ይሉሻል።
[21]በልብሽም እንዲህ ትያለሽ፣
‘እነዚህን የወለደልኝ ማን ነው?
እኔ ሐዘንተኛና መካን፣
የተሰደድሁና የተጠላሁ ነበርሁ፤
እነዚህን ማን አሳደጋቸው?
ብቻዬን ቀርቼ ነበር፤
ታዲያ፣ እነዚህ ከየት መጡ?’

[22]ልዑል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

“እነሆ፤ አሕዛብን በጥቅሻ እጣራለሁ፤
ዐርማዬንም ለሕዝቦች ከፍ አደርጋለሁ፤
ወንዶች ልጆችሽን በዕቅፋቸው
ያመጡልሻል፤
ሴቶች ልጆችሽንም በትከሻቸው
ይሸከሙልሻል።
[23]ነገሥታት አሳዳጊ አባቶችሽ፣
እቴጌዎቻቸው ሞግዚቶችሽ ይሆናሉ፤
በግንባራቸው ተደፍተው ይሰግዱልሻል፤
የእግርሽን ትቢያ ይልሳሉ፤
አንቺም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ
ታውቂያለሽ፤
እኔን ተስፋ የሚያደርጉም አያፍሩም።”

[24]ከተዋጊ ብዝበዛ ማስጣል፣
ከጨካኝስ[T] ምርኮኞችን ማዳን ይቻላልን?

[25]እግዚአብሔር ግን እንዲህ ይላል፤
“ከተዋጊዎች ላይ ምርኮኞች በእርግጥ
ይወሰዳሉ፤
ከጨካኞችም ላይ ምርኮ ይበዘበዛል፤
ከአንቺ ጋር የሚጣሉትን እጣላቸዋለሁ፤
ልጆችሽንም እታደጋለሁ።
[26]አስጨናቂዎችሽ የራሳቸውን ሥጋ እንዲበሉ
አደርጋቸዋለሁ፤
በወይን ጠጅ እንደሚሰከር ሁሉ፣ በገዛ
ደማቸው ይሰክራሉ።
ከዚያም የሰው ዘር ሁሉ፣
እኔ እግዚአብሔር አዳኝሽ፣
ታዳጊሽም የያዕቆብ ኀያል እንደ ሆንሁ
ያውቃል።”

## የእስራኤል ኀጢአትና የእግዚአብሔር ባሪያ ታዛዥነት

# 50

እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“እናታችሁን የፈታሁበት
የፍቺ ወረቀት የት አለ?
ወይስ እናንተን የሸጥኋችሁ
ለየትኛው አበዳሪዬ ነው?
እነሆ፤ ስለ ኀጢአታችሁ ተሸጣችኋል፤
ስለ መተላለፋችሁም እናታችሁ ተፈታለች።
[2]በመጣሁ ጊዜ ለምን በዚያ ሰው አልነበረም?
በተጣራሁስ ጊዜ የሚመልስ ሰው እንዴት
በዚያ ታጣ?
ስለ እናንተ ወጆ ለመክፈል ክንዴ አጥራ ነበርን?
እናንተንስ ለማዳን ኀይል አነሰኝን?
እነሆ፤ በተግሣጼ ባሕሩን አደርቃለሁ፤
ወንዞችን ምድረ በዳ አደርጋለሁ፤
ዓሦቻቸው ውሃ በማጣት ይሸታሉ፤
በጥማትም ይሞታሉ።

ኢሳ41፥28፤59፥1፤ኤር14፥9

49፥19 ዘሌ26፥33፤ ኢሳ1፥20፤5፥6፤54፥1:3፤60፥18፤62፥4፤ ሕዝ36፥10-11፤ ዘካ10፥10
49፥20 ኢሳ54፥1-3፤ ዘካ2፥4፤10፥10
49፥21 መዝ142፥4፤ ኢሳ1፥8፤5፥13፤29፥23፤ 47፥8፤51፥18፤54፥1:6፤60፥8፤66፥7-8፤ ኤር10፥20
49፥22 ዘፍ15፥2፤ ኢሳ11፥10:12፤14፥2፤ ሉቃ15፥5
49፥23 ዘፍ3፥14፤ 27፥29፤ዘፀ6፥2፤ ዘኍ11፥12፤ መዝ22፥5:23፤37፥9፤ 72፥9፤130፥5፤ ኢሳ29፥22፤41፥11፤ 42፥8፤ 60፥3:10-11:16፤ራእ3፥9
49፥24 ማቴ12፥29፤ ማር3፥27፤ሉቃ11፥21
49፥25 1ሳሙ24፥15፤ ኢሳ13፥11፤14፥2፤ 25፥4:5:9፤33፥22፤ 35፥4፤43፥26፤51፥22፤ ኤር50፥33-34፤ ማር3፥27
49፥26 ዘፍ49፥24፤ ዘፀ6፥7፤ዘኍ23፥24፤ ኢዮ19፥25፤መዝ132፥2፤ ኢሳ9፥4:20፤11፥9፤ 13፥11፤25፥9፤48፥17፤ ኤር25፥27፤ሕዝ39፥7፤ ናሆ1፥10፤3፥11፤ ራእ16፥6
50፥1 ዘዳ24፥1፤ 32፥30፤መሳ3፥8፤ ነህ5፥5፤ኢሳ1፥28፤ ሆሴ2፥2፤ማቴ18፥25፤ 19፥7፤ማር10፥4
50፥2 ዘፍ18፥14፤ ዘፀ14፥22፤ዘኍ11፥23፤ 1ሳሙ8፥19፤ መዝ18፥15፤68፥35፤ 107፥33፤

[T]24 የሙት ባሕር ጥቅልሎች፣ ሱልጌትና የሱርስቱ ቅጅ (እንዲሁም የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም ቍ25 ይመ) ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ *ከጻድቅስ* ይላል።

49፥19-20 *በጣም ጠበናል፤* እስራኤል እንደ ገና ተመልሳ መቋቋሟ አስደናቂ ነው፤ ተፈጻሚነቱም አይቀሬ ነው። ትንቢቱ ከባቢሎን ምርኮ በተመለሱ ጊዜ በከፊል ተፈጽሞአል (የ11፥11 ማብ ይመ)፤ ወደፊትም ከአይሁድና ከአሕዛብ ወገን በመንፈስ የተወለዱትን የአብርሃም ዘሮች የሚያካትት ነው (54፥17 እና ማብ ይመ)።

49፥19 *ፈራርሰሽ ... ፈጽሞ ቢጠፋ፤* ከቍ8 ጋር ያነጻጽሩ። 44፥26 እና ማብ ይመ።

49፥21 *ሐዘንተኛና መካን፤* እስራኤል ሴት በ54፥1 ላይ እንደ መካን ሴት ተጠቅሳለች።

49፥22 *ዐርማዬንም ... ከፍ አደርጋለሁ፤* 5፥26 እና ማብ ይመ፤ 13፥2 ይመልከቱ። *ወንዶች ልጆችሽን ... ያመጡልሻል፤ ሴቶች ልጆችሽንም፤* 11፥12 እና ማብ ይመ። አሕዛብ እስራኤልን መልሰው እንደሚያመጡ በ14፥2፤ 43፥6፤ 60፥9 ላይ ተጠቅሶአል። *በዕቅፋቸው፤* ከ60፥4 ጋር ያነጻጽሩ፤ 40፥11 እና ማብ ይመ።

49፥23 *ነገሥታት ... ይሰግዱልሻል፤* ቍ7:11፥14 እና ማብ ይመ። *እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቂያለሽ፤* ቍ26፤ 60፥16፤ ሕዝ12፥20፤ 13፥9፤ 36፥38 ይመ። *እኔን ተስፋ የሚያደርጉም፤* 40፥31 እና ማብ ይመ። *አያፍሩም፤* 29፥22 እና ማብ ይመ።

49፥24 *ከተዋጊ ... ከጨካኝስ፤* ባቢሎናውያንን ያመለክታል (51፥13 ይመ)።

49፥25 *ምርኮኞች ... ይወሰዳሉ፤* ዕዝ2፥1:64-65፤ ኤር50፥33-34፤ 52፥27-30 ይመ። *እጣላቸዋለሁ፤* እግዚአብሔር የሕዝቡን ጕዳይ ይመለከታል፤ ይከራከርላቸዋልም (ኤር50፥34)። *እታደጋለሁ፤* 35፥4 እና ማብ ይመ።

49፥26 *አስጨናቂዎችሽ፤* 14፥4፤ 16፥4፤ 51፥13 ይመ። *የራሳቸውን ሥጋ እንዲበሉ፤* ኢየሩሳሌም በባቢሎናውያን በተከበበች ጊዜ የሚበላ ነገር ስለ ጠፋ ሰዎች የሰው ሥጋ እስከ መብላት ደርሰው ነበር (ሰቆ4፥10)። *በገዛ ደማቸው ይሰክራሉ፤* ከ51፥22-23 ጋር ያነጻጽሩ። *የሰው ዘር ሁሉ ... ያውቃል፤* ቍ23 እና ማብ ይመ። *አዳኝሽ፤* 43፥3 እና ማብ፤ 60፥16 ይመ። *ታዳጊሽ፤* 41፥14 እና ማብ ይመ። *የያዕቆብ ኀያል፤* 1፥24 እና ማብ፤ 60፥16 ይመ።

50፥1 *የፍቺ ወረቀት፤* ባል ሚስቱን መፍታት ከፈለገ ይህን ማድረግ ይገባዋል (ዘዳ24፥1:3፤ ማቴ19፥7፤ ማር10፥4 ይመ)። በኤር3፥8 እንደ ተገለጸው እግዚአብሔር ለሰሜኑ የእስራ ኤል መንግሥት የፍቺ ወረቀት ሰጥቶአል፤ ነቢዩ ኢሳይያስም በ54፥6-7 እግዚአብሔር ይሁዳን እንደ ተዋት ተናግሮአል (62፥4 ይመ)። ምናልባት ኢሳይያስ የሚያመለክተው የፍቺ ሐሳብ ከእግዚአብሔር አለመምጣቱን ነው። ይሁዳ ከእግዚአብሔር ጋር የነበራትን ቃል ኪዳን አፍርሳለች፤ ስለዚህ የይሁዳ በምርኮ መወሰድ ፍቺ ሳይሆን፣ ለተወሰነ ጊዜም ቢሆን ከእግዚአብሔር መለየቷን የሚያመለክት ነው (54፥7 ይመ)። *አበዳሪዬ፤* አንድ ሰው ላበደረው ሰው ዕዳውን ካልከፈለ፣ ልጆቹ በባርነት መሸጥ ነበረባቸው (2ነገ4፥1) እግዚአብሔር ግን አበዳሪ የለውም። *የሸጥኋችሁ፤* ከ45፥13፤ 52፥3 ጋር ያነጻጽሩ።

50፥2 *በመጣሁ ጊዜ ... በተጣራሁስ ጊዜ፤* በአገልጋዮቹ በነቢያት አማካይነት ማለት ነው (ኤር25፥4 ይመ)። *የሚመልስ ሰው እንዴት በዚያ ታጣ፤* እግዚአብሔርን ላለመስማት እስራ ኤል ጆሮዋን ደፍና ነበር (6፥10 እና ማብ 66፥4 ይመ)። *ክንዴ አጥራ ነበርን?* ክንድ ኀይልን ያመለክታል። *ባሕሩን አደርቃለሁ፤* ቀይ ባሕርን ተሻግሮ መሄድን ያመለክታል (43፥16-17 እና ማብ፣ መዝ106፥9 ይመ)። *ወንዞችን ምድረ በዳ፤* 42፥15 እና ማብ ይመ። *ዓሦቻቸው ... ይሸታሉ፤* ምናልባት በግብፅ የነበረውን መቅሠፍት የሚያስታውስ ነው (19፥5-6:8፤ ዘፀ7፥18)።

[3]ሰማይን ጨለማ አለብሰዋለሁ፤
ማቅን መሸፈኛው አደርጋለሁ።
[4]ልዑል እግዚአብሔር የተባ አንደበት
ሰጥቶኛል፤
ስለዚህ ደካሞችን ብርቱ ለማድረግ ምን
ማለት እንዳለብኝ ዐውቃለሁ፤
በየማለዳው ያነቃኛል፤
በመማር ላይ እንዳለ ተማሪ ለመስማት
ጆሮዬን ያነቃዋል።
[5]ልዑል እግዚአብሔር ጆሮዬን ከፍቶታል፤
እኔም ዐመፀኛ አይደለሁም፤
ወደ ኋላም አላፈገፈግሁም።
[6]ለሚገርፉኝ ጀርባዬን፣
ጢሜን ለሚነጩ ጒንጩን ሰጠሁ፤
ፊቴን ከውርደት፣
ከጥፋትም አልሰወርሁም።
[7]ልዑል እግዚአብሔር ስለሚረዳኝ
አልዋረድም፤
ስለዚህ ፊቴን እንደ ባልጩት ድንጋይ
አደርጌአለሁ፤
እንደማላፍርም ዐውቃለሁ።
[8]ንጹሕ መሆኔን የሚያረጋግጥልኝ በአጠገቤ አለ፤
ታዲያ ማን ሊከሰኝ ይችላል?
እስቲ ፊት ለፊት እንጋጠም!
ተቃዋሚዬስ ማን ነው?
እስቲ ይምጣ!
[9]የሚረዳኝ እርሱ ጌታ እግዚአብሔር ነው፤
የሚፈርድብኝስ ማን ነው?
እነሆ፤ ሁሉም እንደ ልብስ ያረጃሉ፤
ብልም ይበላቸዋል።

[10]ከእናንተ እግዚአብሔርን የሚፈራ፣
የባሪያውንም ቃል የሚሰማ ማን ነው?
ያ ሰው በጨለማ የሚሄድ ከሆነና፣
ብርሃንም ከሌለው፣
በእግዚአብሔር ይታመን፤
በአምላኩም ይደገፍ።
[11]አሁን ግን እናንት እሳት አንድዳችሁ፣
የራሳችሁን የሚንበለበል ችቦ የያዛችሁ ሁሉ፣
በሉ የእሳት ብርሃን ሂዱ፤
ባንበለበላችሁትም የችቦ ብርሃን ተመላለሱ።
እንግዲህ ከእጄ የምትቀበሉት ይህ ነው፤
በሥቃይም ትጋደማላችሁ።

## የዘላለም ድነት ለጽዮን

**51** "እናንት ጽድቅን የምትከታተሉ፣
እግዚአብሔርን የምትፈልጉ ስሙኝ፤
ተቈርጣችሁ የወጣችሁበትን ዐለት፣
ተቈፍራችሁ የወጣችሁበትንም ጒድጓድ
ተመልከቱ።
[2]ወደ አባታችሁ ወደ አብርሃም፣
ወደ ወለደቻችሁም ወደ ሣራ ተመልከቱ፤
በጠራሁት ጊዜ አንድ ራሱን ብቻ ነበር፤
ባረክሁት፤ አበዛሁትም።
[3]እግዚአብሔር ጽዮንን በእርግጥ ያጽናናታል፤
ፍርስራሾቿንም በርኅራኄ ይመለከታል፤
ምድረ በዳዋን እንደ ዔድን፣
በረሓዋንም እንደ እግዚአብሔር ተክል ቦታ
ያደርጋል፤
ተድላና ደስታ፣
ምስጋናና የዝማሬ ድምፅ በእርሷ ይገኛሉ።

50፥3 ዘፀ10፥22፤ ኢሳ5፥30፤ራእ6፥12
50፥4 ቊ5፤ ዘፀ4፥12፤መዝ5፥3፤ 88፥13፤119፥147፤ 143፥8፤ኢሳ28፥9፤ 40፥29፤61፥1፤ ማቴ11፥28
50፥5 ኢሳ35፥5፤ 48፥16፤ሕዝ2፥8፤ 24፥3፤ማቴ26፥39፤ ዮሐ8፥29፤14፥31፤ 15፥10፤ሐሥ26፥19፤ ዕብ5፥8
50፥6 ዘኍ12፥14፤ 2ሳሙ10፥14፤ ኢሳ53፥5፤ሰቆ3፥30፤ ማቴ26፥67፤27፥30፤ ማር10፥34፤14፥65፤ 15፥19፤ሉቃ22፥63፤ ዮሐ19፥1
50፥7 ኢሳ28፥16፤ 29፥22፤41፥10፤42፥1፤ 48፥16፤ኤር1፥18፤ 15፥20፤ሕዝ3፥8-9
50፥8 ኢዮ13፥19፤ መዝ34፥18፤ኢሳ26፥2፤ 41፥1፤43፥26፤49፥4፤ ሮሜ8፥32-34
50፥9 ኢዮ13፥28፤ ኢሳ41፥10፤48፥16፤ 51፥8፤ሮሜ8፥1፡34
50፥10 መዝ107፥14፤ ምሳ1፥7፤ኢሳ1፥19፤ 10፥20፤26፥4፤49፥3፤ ሐጌ1፥12፤ሐሥ26፥18
50፥11 ዘዳ21፥22-23፤ ኢዮ15፥20፤ምሳ26፥18፡ 27፤ኢሳ1፥31፤ 65፥13-15፤ያዕ3፥6
51፥1 ቊ7፤ ዘዳ7፥13፤16፥20፤ መዝ94፥15፤ኢሳ17፥10፤ 46፥3፤55፥6፤63፥8፤ 65፥10፤ሮሜ9፥30-31

51፥2 ዘፍ12፥2፤17፥6፤ኢሳ29፥22፤ሮሜ4፥16፤ዕብ11፥11
51፥3 ዘፍ2፥8፤መዝ51፥18፤ኢሳ5፥6፤25፥9፤35፥10፤40፥1፤41፥19፤ 44፥26፤52፥9፤61፥4፤65፥18፤66፥10፤ኤር16፥9፤17፥26፤30፥19፤33፥11

50፥3 *ሰማይን ጨለማ፤* ምናልባት ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ በግብፅ ላይ የወረደው የጨለማ መቅሠፍት ለማስታወስ ይሆናል (ዘፀ10፥21)፤ ይሁን እንጂ 13፥10 እና ማብ ይመ።

*50፥4-9* ወይም 4-11፤ ሦስተኛው የአገልጋዩ መዝሙር ነው (የ42፥1-4 ማብ ይመ)።

50፥4 *የተባ አንደበት ሰጥቶኛል፤* በ42፥3 ላይ አገልጋዩ ደካሞችን እንደሚደግፍ ተጠቅሶአል (ከ49፥2 ጋር ያስተያዩ)፤ ከኤር31፥25 ጋር ያነጻጽሩ። *ለመስማት ጆሮዬን ያነቃዋል፤* እግዚአብሔርን ላለመስማት፣ ዐውቃ ጆሮዋን እንደ ደፈነችው እንደ እስራኤል ሳይሆን (ቊ2 ይመ)፣ አገልጋዩ እግዚአብሔርን ለመስማት ንቁ ነበር።

50፥5 *ጆሮዬን ከፍቶታል፤* የመታዘዝ ምልክት (1፥19፤ መዝ40፥6 ይመ)። *ዐመፀኛ አይደለሁም፤* እንደ እስራኤል አልሆንሁም ማለት ነው (1፥2 እና ማብ 1፥20 ይመ)።

50፥6 *ለሚገርፉኝ ጀርባዬን፤* መገረፍ ወይም መመታት ለወንጀለኞች ወይም ለሰነፎች ቢሆንም፣ አገልጋዩ ይህን በፍጹም ታዛዥነት ተቀብሎታል (ምሳ10፥13፤ 19፥29፤ 26፥3፤ ማቴ27፥26፤ ዮሐ19፥1 ይመ)። *ጢሜን ለሚነጩ፤* የመናቅና የማዋረድ ምልክት ነው (2ሳሙ10፥4-5፤ ነህ13፥25 ይመ)። *ከውርደት፣ ከትፋትም፤* ጥላቻን ለመግለጽ (ኢዮ30፥10)፣ ለማስደብ ወይም ለማዋረድ (ዘዳ25፥9፤ ኢዮ17፥6፤ ማቴ27፥30 ይመ) ነው። ይህ ሁኔታ አገልጋዩ ከፍተኛ ሥቃይ እንደሚደርስበት በ52፥13-53፥12 ተጠቅሶአል።

50፥7 *ስለሚረዳኝ፤* ቊ9፤ 49፥8 ይመ። *አልዋረድም ... እንደማላፍርም ዐውቃለሁ፤* 29፥22 እና ማብ ይመ። አገልጋዩ እስከ መጨረሻው ይከብራል (49፥7፤ 52፥13፤ 53፥10-12 ይመ)። *ፊቴን እንደ ባልጩት ድንጋይ፤* አገልጋዩ እንደ ነቢያት ሁሉ በፍጹም ድፍረት ጸንቶ ይቆማል። ኢየሱስ ክርስቶስ በድፍረት በሉቃ9፥51 ወደ ኢየሩሳሌም ፊቱን አቅንቶ ከሄደበት ሁኔታ ጋር ይህን ያነጻጽሩ።

50፥8 *የሚያረጋግጥልኝ፤* እግዚአብሔር ጻድቅ መሆኑን ያረጋግጥለታል (45፥25 ይመ፤ በመጨረሻ ተሟልቶ የሚፈጸም ስለ መሆኑ 1ጢሞ3፥16 ይመ)። *ማን ሊከሰኝ ይችላል፤* 49፥25 እና ማብ ይመ። ክርስቶስ ምንም ኀጢአት የማይገኝበት መሆኑ፣ በእርሱ በሚያምኑት ላይ የሚመጣውን ክስ ሁሉ ሊያስወግድ ይችላል (ሮሜ8፥31-34 ይመ)። *ተቃዋሚዬስ፤* ከ54፥17 ጋር ያነጻጽሩ።

50፥9 *እንደ ልብስ ያረጃሉ፤ ብልም፤* በ51፥8 ላይ እንደ ተገለጸው፣ ጻድቃንን በሐሰት የሚከሱ ብል ይበላቸዋል፤ ይጠፋሉ ማለት ነው።

50፥10 *እግዚአብሔርን የሚፈራ፤* ዘፍ20፥11፤ ምሳ1፥7 እና ማብ ይመ፤ ከ25፥3፤ 59፥19 ጋር ያነጻጽሩ። *በጨለማ፤* ችግር ወይም ጭንቀት ሊሆን ይችላል፤ ይህም አገልጋዩ ከደረሰበት ጋር እጅግ ተመሳሳይ ነው (ከ8፥22 ጋር ያነጻጽሩ)። *ይታመን ... ይደገፍ፤* እንዲህ ዐይነቱን መታመን እግዚአብሔር በ12፥2፤31፥1 ላይ በተጠቀሰው ቃሉ አደፋፍሮአል።

50፥11 *እሳት አንድዳችሁ ... የሚንበለበል ችቦ፤* ምናልባት የክፉዎችን ልምምድ፣ ይህንኑ የሚያደርጉትን ሰዎች የሚያጠፉቸውንም ለማመልከት ነው። እሳት የመቅጫ ምልክት ነው (1፥31 እና ማብ ይመ፤ ከ9፥18፤ 47፥14፤ መዝ7፥13 ጋር ያነጻጽሩ)። *በሥቃይ፤* ከ66፥24 ጋር ያነጻጽሩ።

51፥1 *ጽድቅን የምትከታተሉ፤* ከቊ7፤ ዘዳ16፥20፤ ምሳ15፥9 ጋር ያነጻጽሩ። *ዐለት፤* አብርሃምን ለማለት ነው (ቊ2)፤ በሌላ ቦታ ላይ እግዚአብሔርም፣ "ዐለት" ተብሎአል (17፥10 እና ማብ ይመ)።

51፥2 *አንድ ራሱን ብቻ ነበር፤* ዘፍ12፥1፤ ሕዝ33፥24 ይመ። *ባረክሁት፤ አበዛሁትም፤* ዘፍ12፥2-3፤ 13፥16፤ 15፥5፤ 17፥5፤ 22፥17 ይመ።

51፥3 *ያጽናናታል ... በርኅራኄ፤* 49፥13 እና ማብ ይመ። *ምድረ በዳዋን እንደ ዔድን፤* 35፥1-2 ይመ። በኢል2፥3 ላይ የዔድን ገነት ልምላሜና የምድረ በዳ ባድማነት ተነጻጽረው ተጠቅሰዋል፤ ከዘፍ2፥8፡10 ጋር ያነጻጽሩ። *ተድላና ደስታ፤* ቊ11፤ 25፥9 እና ማብ ይመ።

⁴"ወገኔ ሆይ፤ አድምጠኝ፤
ሕዝቤ ሆይ፤ ስማኝ፤
ሕግ ከእኔ ይወጣል፤
ፍርዴም ለሕዝቦች ብርሃን ይሆናል።
⁵ጽድቄ በፍጥነት እየቀረበ፣
ማዳኔም እየደረሰ ነው፤
ክንዴም ለመንግሥታት ፍትሕን ያመጣል፤
ደሴቶች ወደ እኔ ይመለከታሉ፤
ክንዴንም በተስፋ ይጠብቃሉ።
⁶ዐይኖቻችሁን ወደ ሰማያት አንሡ፤
ወደ ታች ወደ ምድርም ተመልከቱ፤
ሰማያት እንደ ጢስ በነው ይጠፋሉ፤
ምድር እንደ ልብስ ታረጃለች፤
ነዋሪዎቿም እንደ አሸን ፈጥነው ይረግፋሉ፤
ማዳኔ ግን ለዘላለም ይኖራል፤
ጽድቄም መጨረሻ የለውም።

⁷"እናንተ ጽድቅን የምታውቁ፣
ሕጌንም በልባችሁ ያኖራችሁ ሰዎች ስሙኝ፤
ሰዎች ሲዘብቱባችሁ አትፍሩ፤
ሲሰድቧችሁ አትደንግጡ።
⁸ብል እንደ ልብስ ይበላቸዋል፤
ትል እንደ በግ ጠጕር ይውጣቸዋል፤
ጽድቄ ግን ለዘላለም፣
ማዳኔም ከትውልድ እስከ ትውልድ ጸንታ
ትኖራለች።"

⁹*የእግዚአብሔር ክንድ ሆይ፤*
ተነሥ፤ ተነሥ! ኀይልን ልበስ፤
እንዳለፉት ዘመናት፣
በጥንት ትውልዶችም እንደ ሆነው ሁሉ
ተነሥ።
ረዓብን የቈራረጥህ፣
ታላቁን ዘንዶ የወጋህ አንተ አይደለህምን?
¹⁰የዳኑት እንዲሻገሩ ባሕሩን፣
የታላቁን ጥልቅ ውሆች ያደረቅህ፣
በጥልቁም ውስጥ መንገድ ያበጀህ፣
አንተ አይደለህምን?
¹¹*እግዚአብሔር* የተቤዣቸው ይመለሳሉ፤
በዝማሬ ወደ ጽዮን ይገባሉ፤
የዘላለማዊ ደስታን አክሊል ይቀዳጃሉ፤
ተድላና ደስታ ያገኛሉ፤
ሐዘንና ልቅሶም ከእነርሱ ይሸሻል።

¹²"የማጽናናችሁ እኔ፣ እኔው ብቻ ነኝ፤
ሟች የሆኑትን ሰዎች፣
እንደ ሣር የሚጠወልጉትን የሰው ልጆች
ለምን ትፈራለህ?
¹³የፈጠረህን፣
ሰማያትን የዘረጋውን፣
ምድርን የመሠረተውን *እግዚአብሔርን* ረስተሃል፤
ሊያጠፋህ ከተዘጋጀው፣
ከጨቋኙ ቍጣ የተነሣ፣
በየቀኑ በሽብር ትኖራለህ፤
ታዲያ የጨቋኙ ቍጣ የት አለ?
¹⁴ ዐንገታቸውን የደፉ እስረኞች በፍጥነት
ነጻ ይወጣሉ፤
በታሰሩበትም ጕድጓድ ውስጥ አይሞቱም፤
እንጀራ አያጡም።
¹⁵ሞገዱ እንዲተም ባሕሩን የማናውጥ፣
እኔ *እግዚአብሔር* አምላክህ ነኝና፤
ስሙም የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* ነው።
¹⁶ቃሌን በአፍህ አኖርሁ፤
በእጄ ጥላ ጋረድሁህ፤
ሰማያትን በስፍራቸው ያስቀመጥሁ፣
ምድርን የመሠረትሁ፣
ጽዮንንም፣ 'አንቺ ሕዝቤ ነሽ' ያልሁ እኔ ነኝ።

## *የእግዚአብሔር የቍጣ ጽዋ*

¹⁷*ከእግዚአብሔር* እጅ፣
የቍጣውን ጽዋ የጠጣሽ፣
ዝቃጩ እንኳ ሳይቀር፣
ሰዎችን የሚያንገደግደውን ዋንጫ የጨለጥሽ፣

51፥4 ዘፀ6፥7፤ ዘዳ18፥18፤መዝ50፥7፤ 78፥1፤ኢሳ2፥4፤3፥15፤ 26፥18፤49፥6፤63፥8፤ 64፥9
51፥5 ዘፍ49፥10፤ መዝ37፥9፤85፥9፤ 98፥1፤ኢሳ11፥11፤ 12፥2፤35፥4፤40፥10፤ 50፥2፤52፥10፤59፥16፤ 63፥1፡5
51፥6 ቍ8፤ መዝ37፥20፤89፥33፤ 102፥25-26፤119፥89፤ ኢሳ12፥2፤54፥10፤ ማቴ24፥35፤ ሉቃ21፥33፤ ዕብ1፥10-12፤ 2ጴጥ3፥10
51፥7 ቍ1፤ ዘዳ6፥6፤መዝ119፥11፡ 39፤ኢሳ50፥7፤54፥4፤ ማቴ5፥11፤ሉቃ6፥22፤ ሐሥ5፥41
51፥8 ቍ6፤ ኢዮ13፥28፤ ኢሳ14፥11፤ያዕ5፥2
51፥9 ዘፍ18፥14፤ ዘፀ6፥6፤ዘዳ4፥34፤ 32፥7፤መሳ5፥12፤ ኢዮ9፥13፤መዝ65፥6፤ 68፥30፤74፥13፤98፥1፤ ኢሳ30፥30፤33፥2፤ 40፥31፤52፥1
51፥10 ዘፀ14፥22፤ 15፥5፡8፡13፤ኢዮ36፥30፤ ዘካ10፥11፤ራእ16፥12
51፥11 መዝ109፥28፤ ኢሳ30፥19፤35፥9፤ 44፥23፤48፥20፤ 65፥14፤ኤር30፥19፤ 31፥13፤33፥11፤ ሶፎ3፥14፤ራእ7፥17
51፥12 2ቆሮ1፥15፤ ኢሳ2፥22፤15፥6፤ 40፥1፡6-7፤2ቆሮ1፥4፤ 1ጴጥ1፥24
51፥13 ዘፍ1፥1፤ ኢዮ4፥17፤8፥13፤ ኢሳ7፥4፤9፥4፤17፥7፡ 10፤45፥11፤48፥13፤ 54፥5
51፥14 ኢሳ42፥7፤ 49፥10 51፥15 ዘፀ14፥21፤መዝ93፥3፤ ኢሳ13፥4 51፥16 ዘፀ4፥12፡15፤ 33፥22፤ኢሳ48፥13፤ኤር7፥23፤ 11፥4፤ 24፥7፤ሕዝ14፥11፤ ዘካ8፥8 51፥17 ቍ20፡22፡23፤ መሳ5፥12፤ኢዮ21፥20፤መዝ16፥5፤60፥3፤75፥8፤ኢሳ42፥25፤52፥1፤ 66፥15፤ማቴ20፥22፤ ራእ14፥10፤16፥19

51፥4 *ሕግ ... ፍርዴም፤* የአገልጋዩ አገዛዝ ፍትሕን ያሰፍናል (2፥2-4፤ 42፥4 እና ማብ ይመ)፤ *ለሕዝቦች ብርሃን፤* በ42፥6፤ 49፥6 ላይ አገልጋዩ ብርሃን ተብሏል።

51፥5 *ጽድቄ ... እየቀረበ፤* ከምርኮ ነጻ በሚወጡበት ጊዜ ይህ እውን ይሆናል፤ ድነት በክርስቶስ በኩል ለአሕዛብ ሁሉ በከፍተኛ ደረጃ ይመጣላቸዋል፤ 46፥13 እና ማብ ይመ። *ክንዴም፤* ኀይልን ያመለክታል። *ደሴቶች፤* 11፥11 እና ማብ ይመ። *ወደ እኔ ይመለከታሉ ... በተስፋ፤* 40፥31 እና ማብ 42፥4 እና ማብ ይመ።

51፥6 *ወደ ሰማያት አንሡ፤* 40፥26 ይመ። *ሰማያት ... ይጠፋሉ፤* 34፥4 እና ማብ ይመ። *ምድር እንደ ልብስ ታረጃለች፤* 24፥4፤ ዕብ1፥10-11 ይመ፤ ከኢሳ50፥9 ጋር ያነጻጽሩ። *ለዘላለም ይኖራል፤* ቍ8፤ 45፥17 ይመ። የእግዚአብሔርም ቃል እንዲሁ ለዘላለም ጸንቶ ይኖራል (40፥8 እና ማብ፤ ማቴ24፥35፤ ሉቃ21፥33 ይመ)።

51፥7 *ጽድቅን የምታውቁ፤* ቍ1 እና ማብ ይመ። *ሕጌንም በልባችሁ ያኖራችሁ፤* መዝ37፥31፤ ኤር31፥33 ይመ። *ሲዘብቱባችሁ ... ሲሰድቧችሁ፤* ስለ አገልጋዩ በ50፥6-7 የተጠቀሱትን ይመስላል።

51፥8 *ብል እንደ ልብስ፤* 50፥9 እና ማብ ይመ፤ ከ51፥6 ጋር ያነጻጽሩ።

51፥9፡17 *ተነሥ፤ተነሥ፤* ተመሳሳይ ስለ ሆነው ስለዚህ ጣምራ ትእዛዝ 52፥1 ይቀ (40፥1 እና ማብ ይመ)።

51፥9 *ኀይልን ልበስ፤* ከ50፥2 ጋር ያነጻጽሩ። የ40፥31 ማብ ይመ። *የእግዚአብሔር ክንድ፤* የእግዚአብሔር ኀይል ምልክት ነው (ከቍ5 ጋር ያነጻጽሩ)። 30፥30፤ 50፥2 እና ማብ 52፥10፤ 53፥1፤ 63፥12 ይመ፤ *ረዓብን ... ዘንዶ፤* ግብፅን ነው። የ27፥1፤ 30፥7 ማብ ይመ።

51፥10 *የዳኑት፤* 35፥9 እና ማብ ይመ። *ባሕሩን፤* ቀይ ባሕርን ማለት ነው (50፥2 እና ማብ ይመ)።

*51፥11፤* ይህ ጥቅስ ከ35፥10 ጋር ተመሳሳይ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)።

51፥12 *የማጽናናችሁ፤* ቍ3፤ 49፥13 እና ማብ ይመ። *ሣር፤* 37፥27፤ 40፥6 እና ማብ ይመ።

51፥13 *ሰማያትን የዘረጋውን፣ ምድርን፤* ቍ16፤48፥13 እና ማብ ይመ። *ከጨቋኙ ቍጣ፤* 49፥26 እና ማብ ይመ። የባቢሎን ቍጣ ከኀያሉ ከእግዚአብሔር ቍጣ ጋር ሊወዳደር አይችልም (ከ13፥3፡5፤ 30፥27 ጋር ያነጻጽሩ)።

51፥14 *እስረኞች ... ነጻ ይወጣሉ፤* በባቢሎን ምርኮ ያሉትን ማለት ነው (42፥7 እና ማብ 49፥9 ይመ)። *ጕድጓድ፤* ከ42፥7፤ ኤር37፥16 ጋር ያነጻጽሩ።

51፥15 *ባሕሩን የማናውጥ፤* ከኢዮ26፥12፤ መዝ107፥25፤ ኤር31፥35 ጋር ያነጻጽሩ። *የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 13፥4 እና ማብ ይመ።

51፥16 *ቃሌን፤* በቍ7 ላይ የተገለጸውን የሙሴን ሕግ ማለት ነው። በ49፥2 ላይ እንደ ተገለጸው አገልጋይ ሕዝቡ ለእግዚአብሔር ቃል ምላሽ ሰጥተዋል (ከ59፥21፤ ኢሱ1፥8 ጋር ያነጻጽሩ)። *በእጄ ጥላ፤* 49፥2 እና ማብ ይመ። *ሰማያትን... ያስቀመጥሁ፣ ምድርን፤* ቍ13 እና ማብ ይመ።

51፥17 *የቍጣውን ጽዋ፤* ቍ20-22፤ 13፥3 እና ማብ ይመ።

ኢየሩሳሌም ሆይ፤ ተነሺ፤
ተነሺ፤ ተነሺ።
[18]ከወለደቻቸው ወንዶች ልጆች ሁሉ፣
የመራት አንድም አልነበረም፤
ካሳደገቻቸው ወንዶች ልጆች ሁሉ፣
እጇን ይዞ የወሰዳት ማንም አልነበረም።
[19]እነሆ፤ በጥፋት ላይ ጥፋት መጥተውብሻል፤
ታዲያ ማን ያጽናናሻል?
እነርሱም መፈራረስና ጥፋት፣ ራብና ሰይፍ ናቸው፤
ታዲያ ማን ያስተዛዝንሽ?[ሀ]
[20]ወንዶች ልጆችሽ ዝለዋል፤
በወጥመድ እንደ ተያዘ ሚዳቋ፣
በየጐዳናው አደባባይ ላይ ተኝተዋል።
የእግዚአብሔር ቍጣ፣
የአምላክሽም ተግሣጽ ሞልቶባቸዋል።

[21]ስለዚህ አንቺ የተጐዳሽ፣
ያለ ወይን ጠጅ የሰከርሽ ይህን ስሚ።
[22]ሕዝቡን የሚታደግ አምላክሽ፣
ልዑል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፤ ከእጅሽ፣
ያንገደገደሽን ጽዋ ወስጃለሁ፤
ያንን ጽዋ፣ የቍጣዬን ዋንጫ፣
ዳግም አትጠጪውም፤
[23]ባስጨነቁሽ፣
'በላይሽ ላይ እንድንሄድ ተነጠፊልን'
ባሉሽ እጅ ላይ አደርገዋለሁ፤
ጀርባሽን እንደ መሬት፣
እንደ መሸጋገሪያም መንገድ አደረግሽላቸው።"

# 52

ጽዮን ሆይ፤ ተነሺ፤ ተነሺ፤
ኀይልን ልበሺ፤
ቅድስቲቱ ከተማ፤ ኢየሩሳሌም ሆይ!
የክብር ልብስሽን ልበሺ፤
ያልተገረዘ የረከሰም
ከእንግዲህ ወደ አንቺ አይገባም።
[2]ትቢያሽን አራግፊ፤
ኢየሩሳሌም ሆይ፤ ታንሺ በዙፋንሽ ላይ ተቀመጪ፤
ምርኮኛዪቱ የጽዮን ልጅ ሆይ፤
የዐንገትሽን የእስራት ሰንሰለት አውልቀሽ ጣዪ።

[3]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"ያለ ዋጋ ተሸጣችሁ ነበር፤
ያለ ገንዘብ ትቤዣላችሁ።"

[4]ልዑል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"በመጀመሪያ ሕዝቤ ይኖር ዘንድ ወደ ግብፅ ወረደ፤
በኋላም አሦር ያለ ምክንያት አስጨንቆ ገዛው።

[5]"አሁን እዚህ ምን አለኝ?" ይላል እግዚአብሔር፤
"ሕዝቤ ያለ ምክንያት ተወስዶአል፤
የገዢቻው ተሣልቀውባቸዋል"[ለ]
ይላል እግዚአብሔር።
"ቀኑን ሙሉ፣
ስሜ ያለ ማቋረጥ ይሰደባል።
[6]ስለዚህ ሕዝቤ ስሜን ያውቃል፤
በዚያ ቀንም፣
አስቀድሜ የተናገርሁ እኔ መሆኔን ይረዳል፤
እነሆ፤ እኔው ነኝ።"

[7]በተራሮች ላይ የቆሙ፣
የምሥራች ይዘው የሚመጡ እግሮች፣
ሰላምን የሚናገሩ፣
መልካም ዜና የሚያበስሩ፣

1ዜና16፥31፤መዝ97፥1፤ኢሳ40፥9፤ 42፥11፤ናሆ1፥15፤ሉቃ2፥14፤ ሮሜ10፥15፤1ቆሮ15፥24-25፤ኤፌ6፥15

[ሀ]19 የሙት ባሕር ጥቅሎች፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጉም፣ የቩልጌትና የሱርስቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ ታዲያ እንዴት አስተዛዝንሻለሁ ይላል።
[ለ]5 የሙት ባሕር ጥቅሎችና ቩልጌት ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ ሙሾ ይላል።

51፥18 ኢዮ31፥18፤ መዝ88፥18፤ ኢሳ41፥13፤49፥21
51፥19 ኢሳ14፥30፤ 40፥2፤47፥9፤49፥13፤ 54፥11፤60፥18፤62፥4፤ ኤር14፥12፤15፥5፤ 24፥10፤48፥3፤ ሰቆ3፥47፤ናሆ3፥7
51፥20 ቍ17፤ ዘዳ28፥20፤ ኢዮ18፥10፤40፥11፤ ኢሳ5፥25፤ኤር14፥16፤ 44፥6፤ሰቆ2፥19
51፥21 ቍ17፤ ኢሳ14፥32፤29፥9
51፥22 ቍ17፤ ኢሳ49፥25፤ኤር25፥15፤ 51፥7፤ዕን2፥16፤ ማቴ20፥22
51፥23 ቍ17፤ ኢሱ10፥24፤ መዝ66፥12፤ኢሳ14፥4፤ 49፥26፤ኤር25፥15-17፡ 26፡28፤49፥12፤ ሚክ7፥10፤ዘካ12፥2
52፥1 ዘፍ34፥14፤ ዘፀ28፥2፡40፤ 1ሳሙ2፥4፤ነህ11፥1፤ አስ6፥8፤መዝ110፥3፤ ኢሳ1፥26፤35፥8፤ 49፥18፤51፥9፡17፤ 61፥10፤ኢዩ3፥17፤ ናሆ1፥15፤ዘካ3፥4፤ 9፥8፤ማቴ4፥5፤ ራእ21፥2፡27
52፥2 መዝ9፥14፤ 81፥6፤ኢሳ10፥27፤ 29፥4፤60፥1
52፥3 መዝ44፥12፤ ኢሳ1፥27፤45፥13፤ 1ጴጥ1፥18
52፥4 ዘፍ46፥6፤ ኢሳ10፥24
52፥5 ኢሳ37፥23፤ ሮሜ2፥24
52፥6 ዘፀ6፥3፤ ኢሳ10፥20፡41፥26፤ 49፥23
52፥7 2ሳሙ18፥26፤

የእግዚአብሔርን የቍጣ ፍርድ ደጋግሞ መለማመድ ብዙውን ጊዜ ብርቱ የወይን ጠጅ ጠጥቶ እንደ መስከር ይቈጠራል። ይህ ደግሞ የከፉ መንግሥታት ዕጣ ፈንታ ነው። 29፥9፤ 63፥6፤ መዝ60፥3፤ 75፥8፤ ኤር25፥15-16፤ ሰቆ4፥21፤ ሕዝ23፥32-34፤ ዕን2፥16፤ ዘካ12፥2 ይመ፤ ከዮሐ18፥11 ጋር ያነጻጽሩ።

*51፥18፤* ልጆች የታመሙና የደከሙ ወላጆቻቸውን መርዳትና መንከባከብ ይገባቸዋል።

51፥19 *ማን ያጽናናሻል?* በኤር15፥5 ላይ ተጠቅሶአል፤ ከቍ3 ጋር ያነጻጽሩ።

51፥20 *በወጥመድ እንደ ተያዘ፤* ከምሳ7፥22 ጋር ያነጻጽሩ። *ተግሣጽ፤* 17፥13፤ 54፥9 66፥15 ይመ።

51፥21 *የተጐዳሽ፤* ኢየሩሳሌምን ነው (54፥11 ይመ)። *የሰከርሽ፤* በእግዚአብሔር ቍጣ ማለት ነው (ቍ17 እና ማብ ይመ)።

51፥22 *ሕዝቡን የሚታደግ፤* 49፥25 እና ማብ ይመ። *የቍጣዬን ዋንጫ፤* ቍ17 እና ማብ ይመ።

51፥23 *ባስጨነቁሽ፤* ባቢሎናውያንን ይመለከታል፤ ቍ13-14፡14፥4 ይመ። *ጀርባሽን እንደ መሬት፤* ምናልባት አባባሉ ዘይቤያዊ ይሆናል፤ ይሁን እንጂ ከኢሱ10፥24 ጋር ያነጻጽሩ።

52፥1 *ተነሺ፤ ተነሺ፤ ኀይልን ልበሺ፤* 51፥9፡17 እና ማብ ይመ። *የክብር ልብስሽን፤* የ"ቅድስቲቱን ከተማ" የኢየሩሳሌምን ክህነት ልብስ ማመልከቱ ሊሆን ይችላል፤ 49፥18 እና ማብ ይመ። *ቅድስቲቱ ከተማ፤* 48፥2 እና ማብ ይመ። *ያልተገረዘ የረከሰም፤* ከውጪ የመጡ ወራሪዎችን ነው፤ 35፥8 እና ማብ፤ መሳ14፥3 እና ማብ ይመ።

52፥2 *ትቢያሽን አራግፊ፤* ይህን በ47፥1 ላይ እንደ ተጻፈው በባቢሎን ላይ ከደረሰው ጋር ያነጻጽሩ (የዚያኑ ማብ ይመ)። *የጽዮን ልጅ ሆይ፤* ነቢዩ ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን በሚጠራበት ሰውኛ ዘይቤ የተቀመጠ ሐረግ። *አውልቀሽ ጣዪ፤* 42፥7 እና ማብ 49፥9፤51፥14 ይመ።

52፥3 *ያለ ዋጋ ተሸጣችሁ፤* ጠላት ኢየሩሳሌምን ለማግኘት ለእግዚአብሔር የከፈለው ነገር የለም። 45፥13፤ 50፥1 እና ማብ ይመ። *ያለገንዘብ ትቤዣላችሁ፤* 41፥14 እና ማብ 43፥1፤ 45፥13 ይመ።

52፥4 *አሦር ... አስጨንቆ ገዛው፤* 9፥4 እና ማብ ይመ።

*52፥5፤* በሮሜ2፥24 ላይ በከፊል ተጠቅሶአል። *ያለ ምክንያት፤* ቍ3 እና ማብ ይመ። *ስሜ ... ይሰደባል፤* ሕዝቡ ተማርኮ መወሰዱ፣ የኢየሩሳሌም አምላክ ስም እንዲናቅ አድርጎአል (ሕዝ36፥20-23 ይመ)፤ በ37፥23-24 ላይ አሦራውያን ከተናገሩት የስድብ ቃል ጋር ያነጻጽሩ።

52፥6 *ስሜን ያውቃል፤* 49፥26 እና ማብ ይመ። *በዚያ ቀን፤* ከባቢሎን ምርኮ ነጻ የሚወጡበትን ዕለት የሚያመለክት ነው፤ 10፥20፡27 እና ማብ ይመ። *አስቀድሜ የተናገርሁ፤* ከምርኮ የሚመለሱ ስለ መሆናቸው።

52፥7 *የምሥራች ይዘው የሚመጡ እግሮች፤* የአንድን የጦር ግንባር የውጊያ ውጤት ለመስማት በጕጉት ለሚጠብቅ ንጉሥና ለሕዝቡ ዜናውን ለማድረስ ትንፋሻቸው እስኪቈረጥ የሚሮጡትን መልክተኞች ይመለከታል (2ሳሙ18፥26 ይመ)። እዚህ ላይ ዜናው የሚያመለክተው ከምርኮ የመመለሱን የምሥራች ነው (9ቍ11-12፤ 40፥9 እና ማብ 41፥27)፤ ይህ ቃል ክርስቶስ ከኀጢአት ባርነት ነጻ የሚያወጣ መሆኑንም ያሳያል ሮሜ10፥15፤ ኤፌ6፥15 ይመ።

ድነትን የሚያውጁ፣
ጽዮንንም፣
"አምላክሽ ነግሦአል" የሚሉ እንዴት ያማሩ
ናቸው::
[8]ስሚ፤ ጠባቂዎችሽ ድምፃቸውን ከፍ አድርገዋል፤
በአንድነት በእልልታ ይዘምራሉ::
እግዚአብሔር ወደ ጽዮን ሲመለስ፣
በዐይኖቻቸው ያያሉ::
[9]እናንት የኢየሩሳሌም ፍርስራሾች፣
በአንድነት በእልልታ ዘምሩ፤
እግዚአብሔር ሕዝቡን አጽናንቶአል፤
ኢየሩሳሌምንም ተቤዥቶአልና::
[10]እግዚአብሔር በመንግሥታት ሁሉ ፊት፣
የተቀደሰ ክንዱን ይገልጣል፤
በምድር ዳርቻዎች ያሉ ሁሉ፣
የአምላካችንን ማዳን ያያሉ::

[11]እናንት የእግዚአብሔርን ዕቃ የምትሸከሙ፣
ተለዩ፤ ተለዩ፤ ከዚያ ውጡ፤
ርኩስ ነገር አትንኩ፤
ከዚያ ውጡ ንጹሓንም ሁኑ::
[12]ሆኖም በችኰላ አትወጡም፤
ሸሽታችሁም አትሄዱም፤
እግዚአብሔር ፊት ፊታችሁ ይሄዳል፤
የእስራኤል አምላክ ደጀን ይሆናችኋል::

## የባሪያው ሥቃይና ክብር

[13]እነሆ፤ ባሪያዬ የሚያከናውነው
በማስተዋል ነው፤*
ገናና ይሆናል፤ ከፍ ከፍ ይላል፤ እጅግ
ይከብራልም::
[14]ብዙዎች በእርሱ** እስኪደነግጡ ድረስ፣
መልኩ ከማንም ከሰው የተለየ፤
ከሰው ልጆችም ሁሉ ይልቅ ተጐሳቍሏል::
[15]ስለዚህ ብዙ መንግሥታትን ያስደንቃል፤
በእርሱ ምክንያት ነገሥታት አፋቸውን
ይይዛሉ፤
ያልተነገራቸውን ያያሉ፤
ያልሰሙትን ያስተውላሉ::

**53** የሰማነውን ነገር ማን አመነ?
*የእግዚአብሔርስ ክንድ ለማን ተገለጠ?*
[2]በፊቱ እንደ ቡቃያ፣
ከደረቅም መሬት እንደ ወጣ ሥር በቀለ፤
የሚስብ ውበት ወይም ግርማ የለውም፤
እንድንወደውም የሚያደርግ መልክ
አልነበረውም::
[3]በሰዎች የተናቀና የተጠላ፣
የሕማም ሰውና ሥቃይ ያልተለየው ነበር::
ሰዎች ፊታቸውን እንደሚያዞሩበት
ዐይነት፣
የተናቀ ነበር፤ እኛም አላከበርነውም::

52፥8 ዘኍ10፥36፤ 1ሳሙ14፥16፤ ኢሳ12፥6፤40፥9፤ 56፥10፤59፥20፤62፥6፤ ኤር6፥17፤31፥6፤ ሕዝ3፥17፤33፥7፤ ዘካ8፥3
52፥9 ዕዝ9፥9፤ መዝ74፥3፤98፥4፤ ኢሳ35፥2፤40፥1፤ 48፥20፤51፥3፤ ሉቃ2፥25
52፥10 ኢሱ4፥24፤ 2ዜና32፥8፤ መዝ44፥3፤67፥2፤ ኢሳ11፥9፤30፥30፤ 66፥18፤ሉቃ2፥30፤ 3፥6
52፥11 ዘኍ8፥6፤ 2ዜና36፥10፤ ኢሳ1፥16፤48፥20፤ 2ቆሮ6፥7፤ 2ጢሞ2፥19
52፥12 ዘፀ12፥11፤ 14፥19፤ሚክ2፥13፤ ዮሐ10፥4
52፥13 ኢሱ1፥8፤ ኢሳ4፥2፤6፥1፤20፥3፤ 57፥15፤ሐሥ3፥13፤ ፊል2፥9
52፥14 ዘሌ26፥32፤ 2ሳሙ10፥4፤ኢዮ2፥12፤ 16፥16፤18፥20
52፥15 ዘሌ14፥7፤ 16፥14-15፤ መሳ18፥19፤ መዝ107፥42፤ ኢሳ49፥7፤ሮሜ15፥21፤ ኤፌ3፥4-5

53፥1 መዝ98፥1፤ኢሳ28፥9፤30፥30፤ ዮሐ12፥38፤ሮሜ10፥16
53፥2 2ነገ19፥26፤ኢዮ14፥7፤ኢሳ4፥2፤11፥10፤52፥14
53፥3 ቍ4፡10፤ዘፀ1፥10፤ዘዳ31፥17፤1ሳሙ2፥30፤መዝ22፥6፤69፥29፤ ኢሳ1፥15፤ማቴ16፥21፤27፥29፤ሉቃ18፥31-33፤ ዮሐ1፥10-11፤ዕብ5፥8

*13 *ወይም ይበለጽጋል*
**14 ዕብራይስጡ፣ *በአንተ* ይላል::

*ድነትን፤* 49፥8 እና ማብ ይመ:: *አምላክሽ ነግሦአል፤* መዝ96፥10 ይመ:: የእግዚአብሔር ሕዝብ ወደ ኢየሩሳሌም መመለሱ እግዚአብሔር የዓለም ገዥ መሆኑን በአጽንዖት ያሳያል (40፥9 እና ማብ ይመ):: በክርስቶስ ዳግም ምጽአት ጊዜ፣ የእግዚአብሔር መንግሥት በሙላት የሚመጣው በክርስቶስ ዳግም ምጽአት ነው (ራእ19፥6 ይመ)::

52፥8 *ጠባቂዎችሽ፤* በኢየሩሳሌም የቅጥር ማማ ላይ ሆነው አሻግሮ በማየት የመልክተኞቹን መድረስ የሚጠባበቁትን ሰዎች (ቃፊሮች) ያመለክታል (ከ62፥6-7፤2ሳሙ18፥24-27 ጋር ያነጻጽሩ)::

52፥9 *በእልልታ ዘምሩ፤* 44፥23 እና ማብ ይመ:: *አጽናንቶአል፤* 49፥13 እና ማብ ይመ:: *ተቤዥቶአልና፤* ቍ3 እና ማብ ይመ::

52፥10 *የተቀደሰ ክንዱን፤* 51፥9 እና ማብ ይመ:: የእግዚአብሔር ክንድ ከመቤዠትና ከድነት ጋር እየተያያዘ ወይም እየተቈራኘ ይገለጻል (ዘፀ6፥6 ይመ):: *በምድር ዳርቻዎች ያሉ ሁሉ፤* በ40፥5 ከተገለጸው "የሰው ዘር ሁሉ" ከሚለው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይ ነው፤ ከ45፥22 ጋር ያነጻጽሩ::

52፥11 *ዕቃ የምትሸከሙ፤* ንጉሥ ቂሮስ ናቡከደነፆር የወሰደውን የቤተ መቅደሱን ዕቃ ወደ ኢየሩሳሌም ይዘው እንዲመለሱ ትእዛዝ ሰጥቶ ነበር (ዕዝ1፥7-11):: ለዕቃዎቹም መጓጓዝ ኀላፊዎቹ ካህናቱና ሌዋውያኑ ነበሩ (ዘኍ3፥6-8፤ 2ዜና5፥4-7 ይመ):: *ተለዩ፤ ተለዩ፤* የ40፥1 ማብ ይመ:: *ርኩስ ነገር፤* የጣዖት አምልኮ መገልገያ ዕቃዎችን የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (ከዘዳ31፥19፤ 35፥2 ጋር ያነጻጽሩ)::

52፥12 *በችኰላ አትወጡም፤* 48፥20 እና ማብ ይመ:: *ፊት ፊታችሁ ይሄዳል... ደጀን ይሆናችኋል፤* ከግብፅ ባርነት ነጻ በወጡ ጊዜ እግዚአብሔር ለእስራኤላውያን እንዳደረገው ማለት ነው (ዘፀ13፥21፤ 14፥19-20፤ ከኢሳ42፥16፤ 49፥10፤ 58፥8 ጋር ያነጻጽሩ)::

*52፥13-53፥12፤* ከአራቱ የአገልጋይ መዝሙሮች ይህ አራተኛውና ረጅሙ የአገልጋይ መዝሙር ነው (42፥1-4 እና ማብ ይመ)፡ በምዕራፍ 40-66 እና በምዕራፍ 40-57 ያለውን እጅግ ጠቃሚና ዕንብርት የሆነውን ክፍል አጣምሮ ይይዛል (የ39፥8 ማብ ይመ)፡ መዝሙሩ በሦስት በሦስት ቍጥሮች የተመደቡ አምስት ክፍሎች አሉት:: ይህም ከብሉይ ኪዳን ይልቅ በአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ተደጋግሞ ተጠቅሶአል፤ "የብሉይ ኪዳን ወንጌል" በሚል መጠሪያም ይታወቃል::

52፥13 *አገልጋዬ፤* የ42፥1 ማብ ይመ፡ *የሚያከናውነው በማስተዋል ነው፤* የእግዚአብሔር በረከት ምልክትና (1ሳሙ18፥14 ይመ) ለእግዚአብሔር ቃል የመታዘዝ ምልክት ነው (ኢሱ1፥8 ይመ):: መሲሑ ንጉሥ "በማስተዋል ይገዛል" (ኤር23፥5)፤ ከ53፥10 ጋር ያነጻጽሩ:: *ገናና ይሆናል፤ ከፍ ከፍ ይላል፤* በኢሳይያስ ራእይ ውስጥ የእግዚአብሔርን ማንነት የሚገልጹ ቃላት ናቸው (6፥1 እና ማብ 57፥15 ይመ):: የክርስቶስ ከፍ ከፍ ማለት በሐሥ 2፥33፤3፥13፤ ኤፌ1፥20-23፤ ፊል2፥9-11 ላይ ተገልጾአል (1ጴጥ1፥10-11 ይመ)::

52፥14 *በእርሱ እስኪደነግጡ፤* የክርስቶስን ስቅለትና ሥቃይ በሚመለከቱበት ጊዜ ለማለት ነው፤ ይህን ከፈረሰችው ከጢሮስ ከተማ ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ (ሕዝ27፥35 ይመ):: *የተጐሳቈለም፤* አቦሉ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ሆኖ ሊቀርብ የማይገባው እንስሳ የሚገለጽበትን ቃል ያመለክታል (ሚል1፥14):: ይህን በአገልጋዩ ላይ ከሚደርስበት አሳፋሪ ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ (50፥6 እና ማብ ይመ):: *የተጐሳቈለም ነበር፤* ከመዝ22፥6 ጋር ያነጻጽሩ:: የደረሰበት ሥቃይ ኢሰብአዊና ዘግናኝ ነበር::

52፥15 *ብዙ መንግሥታትን ያስደንቃል፤* ረጭቶ በማንጻት (ዘሌ14፥7፤ ዘኍ8፥7፤19፥18-19) ወይም በመቀደስ (ዘፀ29፥21፤ ዘሌ8፡11፡30) ሊሆን ይችላል:: *ነገሥታት ... አፋቸውን ይይዛሉ፤* አገልጋዩ በሚደርስበት ሥቃይ ከዚያም በኋላ በሚያገኘው ክብር በመደነቅ ማለት ነው (49፥6-7 እና ማብ ይመ)፤ ከኢዮ21፥5 ጋር ያነጻጽሩ:: *ያልተነገራቸውን ... ያስተውላሉ፤* በሮሜ15፥21 ላይ ተገልጾአል:: ነቢያት የተናገሩትን የትንቢት ቃል ባይሰሙም፣ አገልጋዩ የደረሰበትን ሥቃይና ወዲያውም ከፍ ከፍ ማለቱን ሲመለከቱ ተልእኮው ምን እንደ ነበረ ያስተውላሉ (ከ6፥9-10 ጋር ያስተያዩ)::

*53፥1፤* በሙሉ ወይም በከፊል በዮሐ12፥38፤ ሮሜ10፥16 ላይ ተጠቅሶአል:: *የሰማነውን ነገር፤* በነቢያት አማካይነት ለእስራኤልና ለአሕዛብ የተላለፈውን የድነት የምሥራች ማለት ነው (52፥7፡10 ይመ):: *የእግዚአብሔርስ ክንድ፤* 51፥9 እና ማብ ይመ::

53፥2 *ቡቃያ፤* መሲሑ፣ "ከእሴይ ቍጥቋጥ" ይበቅላል፤ 4፥2፤11፥1 እና ማብ ይመ:: አጀማመሩ አነስተኛ ይሆናል ማለት ነው:: *ሥር፤* 11፥10 እና ማብ ይመ:: *ውበት፤* ይህን ቃል የሚተካው የዕብራይስጡ ቃል በ1ሳሙ16፥18 ላይ ስለ ዳዊት ተነግሮአል፤ ስለዚህ ክርስቶስ ለንግሥና የሚያበቃም ሆነ የሚስብ ውበት አልነበረውም::

53፥3 *የተናቀ፤* 49፥7 እና ማብ ይመ፤ መዝ22፥6 ይመ:: *የተናቀ ... አላከበርነውም፤* የዕብራይስጡ ቃል እንዳለ በ2፥2 ላይ ተገልጾአል (የዚያኑ ማብ ይመ)፤ ከዮሐ1፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ:: *የሕማም፤* የዕብራይስጡ ቃል የአእምሮንም ሆነ የአካል ሕመምን ያሳያል (ቍ4፤ ዘፀ3፥7 ይመ):: *ፊታቸውን እንደሚያዞሩበት ዐይነት፤*

[4]በእርግጥ እርሱ ደዌያችንን ወሰደ፤
ሕመማችንንም ተሸከመ፤
እኛ ግን *በእግዚአብሔር* እንደ ተመታ፣
እንደ ተቀሠፈ፣ እንደ ተሠቃየም ቈጠርነው።
[5]ነገር ግን እርሱ ስለ መተላለፋችን ተወጋ፤
ስለ በደላችንም ደቀቀ፤
በእርሱ ላይ የወደቀው ቅጣት ለእኛ ሰላም
አመጣልን፤
በእርሱም ቍስል እኛ ተፈወስን።
[6]እኛ ሁላችን እንደ በጎች ተቅበዝብዘን ጠፋን፤
እያንዳንዳችንም በየመንገዳችን ነጐድን፤
*እግዚአብሔርም*፣
የሁላችንን በደል በእርሱ ላይ ጫነው።

[7]ተጨነቀ፤ ተሠቃየም፤
ነገር ግን አፉን አልከፈተም፤
እንደ ጠቦትም ለዕርድ ተነዳ፤
በሸላቾች ፊት ዝም እንደሚል በግ፣
አፉን አልከፈተም።
[8]በማስጨነቅና[መ] በፍርድ ተወሰደ፤
ስለ ሕዝቤ ኀጢአት ተመቶ፣
ከሕያዋን ምድር እንደ ተወገደ፣
ከትውልዱ ማን አስተዋለ?
[9]በአፉ ተንኰል ሳይገኝበት፣
ምንም ወንጀል ሳይሠራ፣
አሟሟቱ ከክፉዎች፣
መቃብሩም ከባለጠጎች ጋር ሆነ።

[10]መድቀቁና መሠቃየቱ ግን *የእግዚአብሔር*
ፈቃድ ነበር፤
*እግዚአብሔር* ነፍሱን የኀጢአት መሥዋዕት
ቢያደርገውም እንኳ፣
ዘሩን ያያል፤ ዕድሜውም ይረዝማል፤
*የእግዚአብሔርም* ፈቃድ በእጁ ይከናወናል።
[11]ከነፍሱ ሥቃይ በኋላ፣
የሕይወት ብርሃን[ሠ] ያያል፤ ደስም ይለዋል፤
ጻድቅ ባሪያዬ በዕውቀቱ ብዙዎቹን ያጸድቃል፤
መተላለፋቸውንም ይሸከማል።
[12]ስለዚህ ድርሻውን ከታላላቆች[ረ] ጋር እሰጠዋለሁ፤
ምርኮውን ከኀያላን[ሰ] ጋር ይካፈላል፤
እስከ ሞት ድረስ ሕይወቱን አሳልፎ በመስጠቱ፣
ከክፉ አድራጊዎችም ጋር በመቈጠሩ፣

53፥4 ቍ3፤ ዘፍ12፥17፤ ዘዳ5፥24፤ ሩት1፥21፤ ኢዮ4፥5፤ኤር23፥5-6፤ 25፥34፤ሕዝ34፥23-24፤ ሚክ5፥2-4፤ዘካ13፥7፤ ማቴ8፥17፤ዮሐ19፥7 53፥5 ዘዐ28፥38፤ ዘዳ32፥39፤2ዜና7፥14፤ መዝ22፥16፤34፥18፤ 39፥8፤ኢሳ1፥6፤ 9፥6፤50፥6፤ ማቴ27፥26፤ዮሐ3፥17፤ 19፥1፤ ሮሜ4፥25፤5፥1፤ 1ቆሮ15፥3፤ዕብ9፥28፤ 1ጴጥ2፥24-25 53፥6 ቍ12፤ ዘዐ28፥38፤ 1ሳሙ8፥3፤መዝ95፥10፤ ኢሳ56፥11፤57፥17፤ ሚክ3፥5፤ሮሜ4፥25፤ 1ጴጥ2፥24-25 53፥7 መዝ44፥22፤ ኢሳ49፥26፤ ማቴ27፥31፤ ማር14፥61፤ዮሐ1፥29፤ 1ጴጥ2፥23 53፥8 ቍ12፤ መዝ39፥8፤88፥5፤ ዳን9፥26፤ማር14፥49፤ ሐሥ8፥32-33 53፥9 ኢዮ16፥17፤ ኢሳ42፥1-3፤ ማቴ27፥38:57-60፤ ማር15፥27:43-46፤ ሉቃ23፥32:50-53፤ ዮሐ19፥18:38-41፤ 1ጴጥ2፥22፤ 1ዮሐ3፥5፤ ራእ14፥5 53፥10 ቍ3:5፤ ዘፍ12፥17፤ ዘሌ5፥15፤ኢሱ1፥8፤ መዝ22፥30፤ኢሳ46፥10፤49፥4፤ 55፥11፤ዮሐ3፥17፤ ሐሥ2፥23 53፥11 ዘዐ28፥38፤ ኢዮ33፥30፤ኢሳ6፥7፤ 20፥3፤ዮሐ1፥29፤ 10፥14-18፤ሐሥ7፥52፤ 10፥43፤ሮሜ4፥25 53፥12 ቍ6፤ ዘዐ15፥9፤ መዝ119፥162፤ኢሳ6፥1፤59፥16፤ ማቴ26፥28:38:39:42፤27፥38፤ ማር15፥27፤ሉቃ11፥22፤22፥37፤23፥32፤ሮሜ8፥34፤ፊል2፥9፤ ዕብ9፥28፤ 1ጴጥ2፥24

[መ]8 ወይም፣ *በእስር*
[ሠ]11 የሙት ባሕር ጥቅሎች (እንዲሁም የሰብዓ ሊቃናት ትርጒምን ይመ) ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የማሶሬቱ ቅጅ ግን፣ *የሕይወት ብርሃን* የሚለውን ሐረግ አይጨምርም።
[ረ]12 ወይም፣ *ከብዙዎች ጋር*
[ሰ]12 ወይም፣ *እጅግ ብዙ ከሆኑ ጋር*

1፥15 እና ማብ 8፥17 ይመ።

*53፥4፤* የክርስቶስን የፈውስ አገልግሎት በሚመለከት በማቴ8፥17 ላይ በከፊል ተገልጿል። *ደዌያችንን፤* በሽታ ብዙውን ጊዜ ኀጢአትን የተሞላ ሕይወትንና ይልቁንም የመጀመሪያውን ሰው የአዳምን ባሕርይ ተከትሎ የሚመጣ ውጤት ነው (1፥5-6 እና ማብ ይመ)። *በእግዚአብሔር እንደ ተመታ፤* በከባድ ሕመም ማለት ነው (ዘፍ12፥17፤2ነገ15፥5 ይመ)። ሕዝቡ በተለይም እስራኤላውያን አገልጋዩ የሚሠቃየው በራሱ ኀጢአት ምክንያት ነው በማለት ያስቡ ነበር። *እንደ ተሠቃየም፤* እንደ ተጨነቀ ወይም እንደ ተዋረደ ማለት ነው፤ ቍ7፤ 58፥10 ይመ።

53፥5 *ተወጋ፤* መዝ22፥16፤ ዘካ12፥10፤ ዮሐ19፥34 ይመ። *ደቀቀ፤* በመንፈሱ ማለት ነው (መዝ34፥18 ይመ፤ ከኢሳ57፥15 ጋር ያነጻጽሩ)። *ተፈወስን፤* በዚህ ስፍራ የተገለጸው ቃል፣ "ይቅር ተባልን" ከሚለው ቃል ጋር አንድ ነው (6፥10፤ ኤር30፥17፤ የ1ጴጥ2፥24 ማብ ይመ)።

53፥6 *ጠፋን፤* ከመዝ119፥176፤ ኤር50፥6፤ ሕዝ34፥4-6:16፤ 1ጴጥ2፥25 ጋር ያነጻጽሩ። *የሁላችንን በደል በእርሱ ላይ ጫነው፤* ካህኑ ወደ ዱር በሚለቀው ፍየል ላይ እጆቹን ጭኖ የእስራኤልን ኀጢአት ሁሉ በምሳሌነት በእርሱ ላይ እንደሚያኖር ማለት ነው (ዘሌ16፥21 ይመ)፤ 1ጴጥ2፥24 ይመ።

*53፥7-8፤* ኢትዮጵያዊው ጃንደረባ ከፊልጶስ ጋር ሳለ ያነበባቸው ቍጥሮች እነዚህ ናቸው (ሐሥ8፥32-33)።

53፥7 *ተጨነቀ፤* እንደ እስራኤል ማለት ነው። 49፥26 እና ማብ ይመ። ይህን ቃል ዕብራይስጡ በዘፀ5፥6 ላይ "ባሪያ አስገባሪዎች" ብሎ ተርጒሞታል። *እንደ ጠቦትም ለዕርድ ተነዳ፤* ከመዝ44፥22፤ ራእ5፥6 ጋር ያነጻጽሩ። መጥምቁ ዮሐንስ፣ ኢየሱስ ክርስቶስን፣ "የእግዚአብሔር በግ" ብሎ ጠርቶታል (ዮሐ1፥29-35)። *አፉን አልከፈተም፤* ኢየሱስ ክርስቶስ በሊቃነ ካህናቱና (ሐናና ቀያፋ) በጲላጦስ ፊት (ማቴ27፥12-14፤ ማር14፥60-61፤15፥4-5፤ ዮሐ19፥8-9)፤ እንዲሁም በሄሮድስ ፊት ምንም አልተናገረም (ሉቃ23፥8-9)።

53፥8 *በማስጨነቅና በፍርድ፤* በኢየሱስ ክርስቶስ ላይ የተፈረደው ፍርድ ትክክል አልነበረም። *ትውልዱ፤* ዘር ሳይተኩ መሞት እንደ ትልቅ ጒዳት ይቈጠራል (2ሳሙ18፥18)፤ ከቍ10 ጋር ያነጻጽሩ።

53፥9 *ከክፉዎች፤* የአሟሟቱ ሁኔታ በክፉት ሰዎች አመለካከት አንጻር ሲታይ ከተፈረደባቸው ወንጀለኞች ጋር የሚቀበር መሆኑን ያመለክታል። *ከባለጠጎች፤* ሥርዐት ቀብሩ በክብር አልተፈጸመለትም ለማለት ነው። በዕብራይስጥ ቋንቋ ውጤታማ ከሆነው የቃላት ጨዋታ ጋር በማያያዝ ሌሎች የብሉይ ኪዳን ጸሐፊዎች እንደሚያደርጉት እዚህ ላይ ኢሳይያስ፣ ባለጠጎች የሚበለጽጉት በክፉ መንገድ ከመሆኑም በላይ፣ የሚመኩትና የሚታመኑትም ከእግዚአብሔር ይልቅ በሀብታቸው በመሆኑ ከክፉት ጋር አያይዞ ይገልጣቸዋል (ለምሳሌ መዝ37፥16:35፤ ምሳ18፥23፤ 28፥20፤ ኤር5፥26-27፤ ሚክ6፥10-12 ይመ)። በማቴ27፥57-60 እና በሌሎቹ ወንጌሎች ተጽፎ እንደምናገኘው፣ ባለጠጋው የአርማትያሱ ዮሴፍ በተከበረው በራሱ የመቃብር ቦታ የኢየሱስን ሥጋ ቀበረው፤ ይህን ያደረገው ግን በብዙ ይቅር መባሉን በመረዳቱ (ሉቃ7፥47) ጽኑ ፍቅሩን ለመግለጽ መሆኑ እሙን ነው፤ ስለዚህ አፈጻጸሙ ከትንቢቱ ጋር መስማማት ብቻ ሳይሆን ከዚያም በላይ ነው። *በአፉ ተንኰል ሳይገኝበት፣ ምንም ወንጀል ሳይሠራ፤* አማኞች መከራና ሥቃይ በደረሰባቸው ጊዜ እንዲበረታቱ ለማድረግ ሲል ጴጥሮስ እነዚህን ቃሎች ጠቅሶአቸዋል (1ጴጥ2፥22)።

53፥10 *መድቀቁ፤* ቍ5 እና ማብ ይመ። *የኀጢአት መሥዋዕት፤* ምትክ ከመሆን ወይም ዕዳን ከመክፈል ጋር የተያያዘ መሥዋዕት ሲሆን (ዘሌ5፥16፤ 6፥5)፣ በጳዩ አውራ በግ ይሠዋል (ዘሌ5፥15)። *ዘሩን፤* በተከታታይ የሚነሣውን መንፈሳዊውን ትውልድ የሚያመለክት ነው። *ዕድሜውም ይረዝማል፤* ክርስቶስ ከዘላለም እስከ ዘላለም የሚኖር ነው (9፥7 እና ማብ ይመ)። *ይከናወናል፤* 52፥13 ይመ።

53፥11 *የሕይወት ብርሃን፤* ሐረጉ የክርስቶስን ትንሣኤ የሚያመለክት ነው፤ 1ቆሮ15፥4 ይመ። "የሕይወት" ስለሚለው ቃል ኢዮ33፥28:30፤ መዝ49፥19፤ 56፥13 ይመ። *ደስም ይለዋል፤* በ1፥11 እንደ ተጠቀሰው ምንም ፋይዳ የሌላቸው አያሌ የመሥዋዕት ዐይነቶች ለእግዚአብሔር እንደ ቀረቡ ተጠቅሶአል። በዚህ ስፍራ ግን አንዱ የክርስቶስ መሥዋዕት ፍጹም ደስ የሚያሰኝ እንደ ሆነ ተገልጾአል። *በዕውቀቱ፤* እውነተኛውን አምላክ የመረዳቱ ትክክለኛ/እውነተኛ/ ዕውቀት ማለት ነው (1፥3፤ 6፥9፤ 43፥10፤ 45፥4-5፤ 52፥6፤ 56፥10 ይመ)። የዕውቀት መንፈስ (11፥2) በመሲሑ ላይ ዐርፎአል። *ባሪያዬ፤* 41፥8-9፤ 42፥1 እና ማብ ይመ። *ያጸድቃል፤* ብዙዎች እንዲወድቁ ምክንያት ይሆናል ማለት ነው፤ 5፥23፤ ሮሜ5፥19 እና ማብ ይመ። *ብዙዎቹን፤* 52፥15፤ ዳን12፥3 ይመ።

53፥12 *ከታላላቆች ጋር ... ከኀያላን ጋር፤* በታላቅ ድል ምርኮው ደስ እንደሚለው ንጉሥ፣ እግዚአብሔር ለአገልጋዩ ሽልማት ይሰጠዋል (52፥15 ይመ)። *ምርኮውን ... ይካፈላል፤* እግዚአብሔር ለሚሠቃየው ባሪያው የሚሰጠው ነው (ከ9፥3 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሕይወቱን አሳልፎ በመስጠቱ፤* መሥዋዕት አድርጎ ማለት ነው (ቍ10 ይመ)። *እስከ ሞት ድረስ፤* ፊል2፥8 ይመ። *ከክፉ አድራጊዎችም ጋር በመቈጠሩ፤* ይህ ሐረግ ኢየሱስን በሚመለከት

የብዙዎችን ኀጢአት ተሸከመ፤
ስለ ዐመፀኞችም ማለደ።

**የወደፊቱ የጽዮን ክብር**

**54** “አንቺ መካን ሴት፤
አንቺ ልጅ ወልደሽ የማታውቂ፤
ዘምሪ፤
እልል በዪ፤ በደስታ ጩኺ፤
አንቺ አምጠሽ የማታውቂ፣
ባል ካላት ሴት ይልቅ፣
የፈቷ ልጆች ይበዛሉና” ይላል *እግዚአብሔር*።
[2]“የድንኳንሽን ቦታ አስፊ፤
የድንኳንሽን መጋረጃዎች በትልቁ ዘርጊ፤
ፈጽሞ አትቈጥቢ፤
ገመዶችሽን አርዝሚአቸው፤
ካስማዎችሽንም ቀብቅቢ።
[3]ወደ ቀኝም ወደ ግራም ትስፋፊያለሽ፤
ዘሮችሽ መንግሥታትን ይወርሳሉ፤
በባድማ ከተሞቻቸውም ይኖራሉና።
[4]“አይዞሽ አትፍሪ፤ ኀፍረት አይገጥምሽም፤
ውርደት ስለማይደርስብሽ አትሸማቀቂ፤
የወጣትነት ኀፍረትሽን ትረሺዋለሽ፤
የመበለትነት ስድብሽንም ከእንግዲህ አታስ
ታውሺውም።
[5]ባልሽ ፈጣሪሽ ነውና፤
ስሙም የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* ነው፤
ታዳጊሽ የእስራኤል ቅዱስ ነው፤
እርሱም የምድር ሁሉ አምላክ ይባላል።
[6]እንደ ተናቀች የልጅነት ሚስት፣
ከልብ እንዳዘነችና እንደ ተጠላች ሚስት፣
*እግዚአብሔር* እንደ ገና ይጠራሻል”
ይላል አምላክሽ።
[7]“ለጥቂት ጊዜ ተውሁሽ፤
ነገር ግን በታላቅ ርኅራኄ መልሼ እሰበስብ
ሻለሁ።
[8]ለጥቂት ጊዜ እጅግ ስለ ተቈጣሁ፣
ፊቴን ከአንቺ ሰወርሁ፤
ነገር ግን በዘላለማዊ ቸርነቴ፣
እራራልሻለሁ”
ይላል ታዳጊሽ *እግዚአብሔር*።
[9]“ይህ ለእኔ የኖኅ ውሃ ምድርን ዳግመኛ
እንዳያጥለቀልቃት እንደማልሁበት፣
እንደ ኖኅ ዘመን ነው፤
አሁንም አንቺን ዳግም እንዳልቈጣ፣
እንዳልገሥጽሽም ምያለሁ።
[10]ተራሮች ቢናወጡ፣
ኰረብቶች ከስፍራቸው ቢወገዱ እንኳ፣
ለአንቺ ያለኝ ጽኑ ፍቅር አይናወጥም፤
የገባሁትም የሰላም ቃል ኪዳን አይፈርስም”
ይላል መሐሪሽ *እግዚአብሔር*።
[11]“አንቺ የተጨነቅሽ ከተማ ሆይ፤ በዐውሎ ነፋስ
የተናወጥሽ፣ ያልተጽናናሽም፤
እነሆ፤ በከበሩ ድንጋዮች[a] አስጊጬ
እገነባሻለሁ፤
በሰንፔር ድንጋይም እመሠርትሻለሁ።
[12]ጒልላትሽን በቀይ ዕንቍ፣
በሮችሽን በሚያብረቀርቅ ዕንቍዎች፣
ቅጥሮችሽንም በከበሩ ድንጋዮች እሠራለሁ።
[13]ወንዶች ልጆችሽ ሁሉ *ከእግዚአብሔር* የተማሩ
ይሆናሉ፤
የልጆችሽም ሰላም ታላቅ ይሆናል።

54፥1 ዘፍ21፥6፤ 30፥1፤1ሳሙ2፥5፤ መዝ98፥4፤ ኢሳ49፥19:20፤ 66፥7፤ገላ4፥27
54፥2 ዘፍ26፥22፤ ዘፀ35፥18፤39፥40፤ ኢሳ26፥15፤49፥19-20
54፥3 ዘፍ13፥14፤ ኢዮ12፥23፤ኢሳ14፥2፤ 48፥19፤49፥19፤ 60፥4-11
54፥4 ዘፍ30፥23፤ መዝ25፥7፤119፥39፤ ኢሳ28፥16፤29፥22፤ 41፥11፤ 47፥8፤51፥7፤ ኤር2፥2፤22፥21፤ 30፥10፤ኢል2፥21
54፥5 መዝ95፥6፤ 149፥2፤መሓ3፥11፤ ኢሳ1፥4፤6፥3፤12፥4፤ 48፥17፤49፥7፤51፥13፤ 55፥5፤60፥9፤ኤር3፥14፤ 31፥32፤ሆሴ2፥7:16
54፥6 ቍ6-7፤ ዘፀ20፥14፤ኢሳ1፥4፤ 49፥14-21፤50፥1-2፤ 60፥15፤62፥4:12፤ ኤር44፥2፤ሆሴ1፥10፤ ሚል2፥15
54፥7 ኢዮ14፥13፤ መዝ51፥1፤71፥11፤ ኢሳ26፥20፤27፥8፤ 49፥18
54፥8 ቍ10፤ መዝ25፥6፤92፥2፤ 102፥13፤ኢሳ1፥15፤ 9፥12፤14፥1፤26፥20፤ 48፥17፤55፥3፤60፥10፤ 63፥7፤ሆሴ2፥19
54፥9 ዘፍ8፥21፤ ዘዳ28፥20፤መዝ13፥1፤ 103፥9፤ኢሳ12፥1፤ 14፥24፤49፥18፤ 57፥16፤ኤር3፥5:12፤ ሕዝ39፥29፤ሚክ7፥18
54፥10 ቍ8፤ ዘፍ9፥16፤ ዘፀ34፥10፤ ዘኍ25፥12፤መዝ6፥4፤46፥2፤89፥34፤ኢሳ14፥1፤ 42፥6፤51፥6፤ 55፥7፤ዕብ12፥27፤ ራእ6፥14 54፥11 ዘፀ24፥10፤ 1ዜና29፥2፤ኢዮ28፥6፤ኢሳ14፥32፤28፥2:16፤ 29፥6፤51፥19፤ ራእ21፥18:19-20 54፥12 ራእ21፥21 54፥13 ዘሌ26፥6፤ ኢሳ28፥9፤48፥18፤ ሚክ4፥2፤ዮሐ6፥45፤ ዕብ8፥11

[a]11 በዕብራይስጡ የዚህ ሐረግ ትርጒም በትክክል አይታወቅም።

በሉቃ22፥37 ላይ ተጠቅሶአል። *ማለደ፤* በኤር7፥16፤ ላይ “ጸለየ” ተብሎ ተተርጕሞአል። 27፥18 ላይ ደግሞ “ለመነም” ተብሎ ተተር ጕሞአል። ከ59፥16፤ ዕብ 7፥25 ጋር ያነጻጽሩ።

*54፥1፤* ይህን ጥቅስ ሐዋርያው ጳውሎስ ሣራንና የቃል ኪዳኑን ተስፋ ከስማያዊቷ ኢየሩሳሌም ጋር በማያያዝ ገልጾታል (ገላ4፥26-27)። *መካን ሴት፤* በተለይም በምርኮ ዘመን (49፥21 ይመ) እስራኤልን የምትወክለውን ኢየሩሳሌምን በተመለከተ የተጠቀሰ ነው። መካንነት በመካከለኛው ምሥራቅ እንደ ትልቅ ኀፍረት ይቈጠራል (4፥1 እና ማብ ይመ)። *እልል በዪ፣ በደስታ ጩኺ፤* 12፥6፤ 44፥23፤ 52፥9 እና ማብ ይመ። *ባል፤* 50፥1 እና ማብ ይመ። *የፈቷ ልጆች ይበዛሉና፤* 49፥19-20 እና ማብ ይመ። እስራኤል በሥጋም በመንፈስም ትባረካለች (ከ62፥4 ጋር ያነጻጽሩ)።

*54፥2፤* 26፥15፤ 33፥20 እና ማብ ይመ። *የድንኳንሽን፤* ኢየሩሳሌም በራሷ ድንኳን ውስጥ እንደ ተቀመጠች ሴት ተገልጻለች።

54፥3 *ትስፋፊያለሽ፤* 49፥19-20 እና ማብ ይመ፤ ከዘፍ28፥14 ጋር ያነጻጽሩ። *መንግሥታትን ይወርሳሉ፤* 11፥14፤ 49፥7 እና ማብ ይመ።

54፥4 *ውርደት ስለማይደርስብሽ፤* 29፥22 እና ማብ 45፥17 ይመ። *የወጣትነት ኀፍረትሽን፤* ምናልባት በግብፅ የነበረውን የባርነት ዘመን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል፤ ከኤር31፥19፤ ሕዝ16፥60 ጋር ያነጻጽሩ። *የመበለትነት ስድብሽንም፤* እስራኤል ልክ እንደ መበለት ብቻዋን የነበረችበትን የምርኮ ዘመን የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (ቍ6-7)።

54፥5 *ባልሽ፤* 62፥4-5 ይመ። *ታዳጊሽ የእስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4፤ 41፥14 እና ማብ ይመ።

*54፥6-7፤ እንደ ተናቀች የልጅነት ሚስት … እንደ ተጠላች፤* እስራኤል በምርኮ የነበረችበትን ሁኔታ ያመለክታል (49፥14፤ 50፥1 እና ማብ 62፥4 ይመ)።

54፥7-8፡10 *ርኅራኄ፤* 14፥1፤ 49፥10፡13፤ 51፥3 ይመ።

54፥7 *ለጥቂት ጊዜ፤* እስራኤላውያን በባቢሎናውያን ተማርከው የተጋዙበት ዘመን ከግብፅ ባርነት ጋር ሲነጻጸር ጊዜው አጭር ነበር (26፥20፤ 50፥1 እና ማብ ይመ)።

54፥8 *እጅግ ስለ ተቈጣሁ፤* 9፥12፡17፡21 እና ማብ 60፥10 ይመ። *ፊቴን ከአንቺ ሰወርሁ፤* 1፥15 እና ማብ ይመ። *በዘላለማዊ ቸርነቴ፤* ቍ10፤ 55፥3 እና ማብ ይመ፤ ከ45፥17 ጋር ያነጻጽሩ። *ታዳጊሽ፤* ቍ5 ይመ።

54፥9 *ምድርን ዳግመኛ እንዳያጥለቀልቃት፤* ዘፍ9፥11 እና ማብ ይመ። *እንዳልቈጣ፤* 12፥1 እና ማብ ይመ።

54፥10 *ተራሮች … ቢወገዱ፤* ከ51፥6፤ መዝ46፥2፤ 102፥26-27 ጋር ያነጻጽሩ። *ጽኑ ፍቅር … የሰላም ቃል ኪዳን፤* በ55፥3 ላይ በተመሳሳይ ቃላት እንደ ተገለጸው፣ ኪዳኑ አንድም ከእስራኤል ጋር አሊያም ከዳዊት ጋር የተያያዘ መሆኑን ያመለክታል። ከኤር33፥20-21 ጋር ያነጻጽሩ፤ ዘኍ 25፥11-13 ይመ።

*54፥11-12፤* ከምርኮው መልስ በኋላ የነበረችዋን ኢየሩሳሌም የሚያሳየው ዘይቤያዊ አገላለጽ በራእ21፥10፡18-21 ላይ ስለ አዲሲቱ ኢየሩሳሌም በሚያወሳው ገለጻ ላይ ተስተጋብቶ ይገኛል።

54፥11 *የተጨነቅሽ ከተማ፤* ኢየሩሳሌምን ነው፤ 51፥21 ይመ። *በዐውሎ ነፋስ የተናወጥሽ፤* 28፥2 እና ማብ ይመ። *በከበሩ ድንጋዮች፤* ምናልባት ውሃ ሰማያዊና አረንጓዴ ቀለም የተደባለቀበት ቀለም ያላቸው ዕንቆች ሳይሆኑ አይቀርም። ንጉሥ ሰሎሞንም ቤተ መቅደሱን ሲሠራ በእነዚህ ድንጋዮች ተጠቅሞአል (1ዜና29፥2)። *ሰንፔር፤* ከዘፀ24፥10 ጋር ያነጻጽሩ፤ ሕዝ1፥26፤ 10፥1 ይመ።

54፥12 *ጒልላትሽን፤* በቅጥር ጫፍ ላይ ያሉ ተቀጥላ ጌጦች ናቸው። *ቅጥሮችሽንም፤* ከ26፥1 ጋር ያነጻጽሩ።

54፥13-14 *ሰላም… ጽድቅ፤* 48፥18 እና ማብ ይመ።

54፥13 *ከእግዚአብሔር የተማሩ፤* በ50፥4 ላይ እንደ ተገለጸው የእግዚአብሔር አገልጋይ ማለት ነው። ከኤር31፥34 ጋር ያነጻጽሩ።

[14]በጽድቅ ትመሠረቻለሽ፤
 የግፍ አገዛዝ ከአንቺ ይርቃል፤
የሚያስፈራሽ አይኖርም፤
 ሽብር ከአንቺ ይርቃል፤
 አጠገብሽም አይደርስም።
[15]ማንም ጥቃት ቢያደርስብሽ፣ ከእኔ አይደለም፤
 ጥቃት ያደረሰብሽ ሁሉ ለአንቺ እጁን
  ይሰጣል።

[16]"እነሆ የከሰሉ ፍም እንዲቀጣጠል የሚያ
  ራግበውን፣
 የጦር መሣሪያ የሚያበጀውን፣ አንጥረኛውን
  የፈጠርሁ እኔ ነኝ፤
 ጥፋት እንዲያደርስም የፈጠርሁ እኔ ነኝ
  አጥፊውንም የፈጠርሁ እኔ ነኝ፤
[17] በአንቺ ላይ እንዲደገን የተበጀ መሣሪያ
  ይከሽፋል፤
 የሚከስሽንም አንደበት ሁሉ ትረቺያለሽ፤
እንግዲህ *የእግዚአብሔር* ባሪያዎች ርስት
  ይህ ነው፤
 ከእኔ የሚያገኙትም ጽድቃቸው ይኸው
  ነው፤"
   ይላል *እግዚአብሔር*።

**ጥሪ ለተጠሙ**

**55** እናንት የተጠማችሁ ሁሉ ኑ፤
  እናንት ገንዘብ የሌላችሁ፣
ወደ ውሆች ኑ፤
 ኑና ግዙ፤ ብሉም፤
ኑና ያለ ገንዘብ፣ ያለ ዋጋ፣
 የወይን ጠጅና ወተት ግዙ።
[2]ገንዘባችሁን እንጀራ ባልሆነ ነገር ላይ ለምን
  ታጠፋላችሁ?
 በማያጠግብስ ነገር ላይ ለምን ጉልበታችሁን
  ትጨርሳላችሁ?
ስሙ፤ እኔን ስሙኝ፤ መልካም የሆነውንም ብሉ፤
 ነፍሳችሁም በጥሩ ምግብ ትደሰታለች።
[3]ጆሮአችሁን ከፍታችሁ ወደ እኔ ቅረቡ፤
 ነፍሳችሁም እንድትኖር አድምጡኝ።
ለዳዊት በገባሁት በጽኑ ፍቅሬ፣
 ከእናንተም ጋር የዘላለም ኪዳን አደርጋለሁ።
[4]እነሆ፤ እርሱን ለሕዝቦች ምስክር፣
 መሪ፣ የጦር አዝማችም አድርጌዋለሁ።
[5]እነሆ፤ የማታውቃቸውን መንግሥታት ትጠራለህ፤
 የማያወቁህ መንግሥታት በፍጥነት ወደ
  አንተ ይመጣሉ፤
ምክንያቱም *እግዚአብሔር* አምላክህ፣
 የእስራኤል ቅዱስ፣
 በክብሩ ከፍ ከፍ አድርጎሃል።
[6]*እግዚአብሔር* በሚገኝበት ጊዜ ፈልጉት፤
 ቀርቦም ሳለ ጥሩት።
[7]ክፉ ሰው መንገዱን፣
 በደለኛም ሐሳቡን ይተው።
ወደ *እግዚአብሔር* ይመለስ፤ እርሱም ምሕረት
  ያደርግለታል፤
 ወደ አምላካችን ይመለስ፤ ይቅርታው ብዙ
  ነውና።

[8]"ሐሳቤ እንደ ሐሳባችሁ፣
 መንገዴ እንደ መንገዳችሁ አይደለምና"
  ይላል *እግዚአብሔር*።
[9]"ሰማያት ከምድር ከፍ እንደሚሉ፣
 መንገዴ ከመንገዳችሁ፣
 ሐሳቤም ከሐሳባችሁ እንዲሁ ከፍ ያለ ነው።

54፥14 2ሳሙ7፥10፤ ኢሳ9፥4፤17፥14፤ 26፥21፤ኤር30፥20፤ ሶፎ3፥15፤ዘካ9፥8
54፥15 ኢሳ41፥11-16
54፥16 ኢሳ10፥5፤ 13፥5፤44፥12
54፥17 መዝ17፥2፤ ኢሳ29፥8፤41፥11፤ 56፥6-8፤63፥17፤65፥8፡ 9፡13-15፤66፥14፤ ዘካ1፥20-21
55፥1 ምሳ9፥5፤ መሓ5፥1፤ኢሳ35፥7፤ ኤር2፥13፤ሰቆ5፥4፤ ሕዝ47፥1፡12፤ ሆሴ14፥4፤ዘካ14፥8፤ ማቴ5፥6፤10፥8፤ 13፥44፤ ሉቃ6፥21፤ ዮሐ4፥14፤7፥37፤ 1ጴጥ2፥2፤ራእ3፥18፤ 21፥6፤22፥17
55፥2 መዝ22፥26፤ መክ6፥2፤ኢሳ1፥19፤ 30፥23፤49፥4፤ ኤር12፥13፤ሆሴ4፥10፤ 8፥7፤ሚክ6፥14፤ ሐጌ1፥6
55፥3 ዘፍ9፥16፤ ዘሌ18፥5፤መዝ78፥1፤ ኢሳ54፥8፡10፤ ዮሐ6፥27፤ ሐሥ13፥34፤ ሮሜ10፥5፤ዕብ13፥20
55፥4 1ሳሙ13፥14፤ 2ዜና7፥18፤ኢሳ32፥1፤ ራእ1፥5
55፥5 ኢሳ2፥3፤ 12፥6፤44፥23፤49፥6፤ 54፥5
55፥6 ዘዳ4፥29፤ 2ዜና15፥2፤መዝ32፥ 6፤50፥15፤ኢሳ49፥13፤ 49፥8፤65፥24፤ ኤር29፥12፤
55፥9 ዘኁ23፥19፤ 33፥3፤ሐሥ17፥27፤2ቆሮ6፥1-2
55፥7 2ዜና6፥21፤7፥14፤30፥9፤ ኢሳ1፥18፤32፥7፤40፥2፤44፥22፤54፥10፤59፥7፤ኤር26፥3፤ሕዝ18፥27-28፡32
55፥8 ኢሳ53፥6፤ሚክ4፥12፤ፊል2፥5፤4፥8

54፥14 *የግፍ አገዛዝ ... ሽብር፤* ከ14፥4፤ 38፥18-19 ጋር ያነጻጽሩ።

54፥15 *ለአንቺ እጁን ይሰጣል፤* ቊ3 ይመ።

54፥16 *አጥፊውንም የፈጠርሁ፤* እግዚአብሔር እስራኤልን ለመቅጣት ሲል እንደ አሦርና እንደ ባቢሎን ያሉትን መንግሥታት አስነሣ (10፥5 እና ማብ፤ 33፥1 እና ማብ ይመ)።

54፥17 *አንደበት ሁሉ ትረቺያለሽ፤* በ50፥8-9 ላይ በተጠቀሰው አገልጋይ ላይ ሕጋዊነት ያለው ምንም ዐይነት ክስ ማቅረብ እንደማይቻል ማለት ነው። *የእግዚአብሔር ባሪያዎች፤* ከምዕራፍ 53 በኋላ ኢሳይያስ "ባሪያ" የሚለውን ቃል በነጠላ ቊጥር አይጽፈውም፤ "አገልጋዮች" የሚለው የብዙ ቊጥር ቃል ግን በ63፥17፤ 65፥8-9፡13-15፤ 66፥14 ተጽፎ ይገኛል፤ ከአይሁድም፣ ከአሕዛብም በእግዚአብሔር ያመኑትን ያመለክታል፤ በሌላ አነጋገር የ"አገልጋይ" ዘር የተባሉትን ማለት ነው፤ 53፥10፤ 49፥19-20 እና ማብ ይመ።

*55፥1፤* የተማረኩት ተመልሰው ወደ አገራቸው እንዲገቡ ተጠርተዋል። *የተጠማችሁ፤* መንፈሳዊ ጥማት ቅድሚያ ሊሰጠው የሚገባ ጉዳይ ነው (41፥17፤ 44፥3፤ መዝ42፥1-2፤ 63፥1 ይመ)። *ገንዘብ የሌላችሁ፤* በችግር ጊዜ ውሃ እንኳ ሳይቀር ይሸጣል። (ሰቆ 5፥4)። *ውሆች፤* ዘይቤያዊ አገላለጹ በመንፈስ መታደስን ያመለክታል፤ ይህን በምሳ9፥5 ላይ ጥበብ ከምታደርገው ጥሪ ጋር ያነጻጽሩ። ኢየሱስ ክርስቶስም ሰዎች የሕይወትን ውሃ እንዲጠጡ ተመሳሳይ ጥሪ አቅርቦአል (ዮሐ4፥14፤7፥37 ይመ)። *ያለ ገንዘብ፤* የአገልጋዩ ሞት (53፥5-9) በነጻ ለተሰጠ ሕይወት የተደረገ ክፍያ ነው (ሮሜ6፥23 ይመ)። *የወይን ጠጅና ወተት፤* የበረከት፣ የተድላ ደስታና የጥጋብ ዘመን ምልክቶች ናቸው።

55፥2 *እንጀራ ባልሆነ፤* የሥርዐተ አምልኮ ባዕድ ትርፍራፊ መብሎችን የሚመለከት ሊሆን ይችላል፤ ከዘዳ8፥3 ጋር ያነጻጽሩ። *በጥሩ ምግብ፤* ታላቅ መንፈሳዊ በረከት በትልቅ ግብዣ ይመሰላል (25፥6 እና ማብ፤ መዝ22፥26፤ 34፥8፤ ኤር31፥14 ይመ)።

55፥3 *የዘላለም ኪዳን፤* ለዳዊት በመሲሑ የሚፈጸም ዘላለማዊ መንግሥት ቃል ተገብቶለታል (9፥7፤ 54፥10፤ 61፥8፤ 2ሳሙ7፥14-16 እና ማብ ይመ)። *በጽኑ ፍቅሬ፤* ሕዝቡ እንደ ማይጠፋ የተሰጠ ተስፋ ነው፤ 54፥8 እና ማብ ይመ። የክርስቶስ ከሙታን መነሣትም እግዚአብሔር ለዳዊት የገባለት ቃል ኪዳን መፈጸሙን ያመለክታል (ሐሥ13፥34 ይመ)።

55፥4 *ለሕዝቦች ምስክር፤* ይህ ጥቅስ እግዚአብሔርን በአሕዛብ መካከል ከፍ ከፍ የሚያደርገውን ዳዊትን (መዝ18፥43፡49-50) ወይም የዳዊት ልጅና ለአሕዛብ ብርሃን የሆነውን መሲሑን (42፥6፤41፥6 እና ማብ ይመ) ያመለክታል። *ለሕዝቦች ... መሪ፤* ተመሳሳይ የማዕረግ ስሞች ለዳዊትም (1ሳሙ13፥14፤25፥30)፣ ለመሲሑም (ዳን9፥25) ተነግረዋል።

55፥5 *መንግሥታት ትጠራለህ፤* አሕዛብ ወደ ጽዮንና ወደ እስራኤል አምላክ እንዲመጡ ማድረግ ዋናው የመጽሐፍ ቅዱስ ጭብጥ ነው (ለምሳሌ 2፥3-4፤ 45፥14፤ ዘካ8፥22 እና ማብ ይመ)። *የማያውቁህ፤* የተገላቢጦሽ ነው፤ እስራኤላውያን ወደ ማያውቋቸው አሕዛብ ተበትነው ነበር፤ በአንጻሩም አሕዛብ ወደ እስራኤል እንደሚመጡ ተገልጾአል (ዘዳ28፥36 ይመ)። ሞዓባዊቷ ሩት ዐማቷን ተከትላ ከማታውቀው ሕዝብ ጋር ለመኖር መጥታለች (ሩት 2፥11)። *የእስራኤል ቅዱስ፤* 1፥4፤ 41፥14 እና ማብ ይመ። *በክብሩ ከፍ ከፍ አድርጎሃል፤* 4፥2፤ 60፥9 ይመ። ሕዝቡ በመንፈስም በሥጋም ይባረካል።

55፥6 *እግዚአብሔር ... ፈልጉት፤* ኤር29፥13-14፤ ሆሴ3፥5፤ አሞ5፥4፡6፡14 ይመ።

55፥7 *ክፉ ሰው ... ይተው፤* 1፥16 ይመ። *ወደ እግዚአብሔር ይመለስ፤ ... ምሕረት ይደረግለታል፤* 43፥25 እና ማብ፤ 44፥22 እና ማብ ይመ።

55፥9 *መንገዴ ... ከፍ ያለ ነው፤* መዝ145፥3 ይመ።

[10]ዝናምና በረዶ
ከሰማይ ወርዶ፣
ምድርን በማራስ፣
እንድታበቅልና እንድታፈራ
ለዘሪው ዘር፣ ለበላተኛም እንጀራ እንድትሰጥ
ሳያደርግ፣
ወደ ላይ እንደማይመለስ ሁሉ፣
[11]ከአፌ የሚወጣውም ቃሌ፣
በከንቱ ወደ እኔ አይመለስም፤
ነገር ግን የምሻውን ያከናውናል፤
የተላከበትንም ዐላማ ይፈጽማል።
[12]በደስታ ትወጣላችሁ፤
በሰላምም ትሸኛላችሁ፤
ተራሮችና ኰረብቶች፣
በፊታችሁ በእልልታ ይዘምራሉ፤
የሜዳ ዛፎች ሁሉ፣
ያጨበጭባሉ።
[13]በእሾኽ ፈንታ የጥድ ዛፍ፣
በኵርንችት ፈንታ ባርሰነት ይበቅላል።
ይህም የእግዚአብሔር መታሰቢያ፣
ሊጠፋ የማይችል፣
የዘላለም ምልክት ይሆናል።"

## ለሌሎች የተሰጠ ድነት

**56** እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"ፍትሕን ጠብቁ፤
መልካሙን አድርጉ፤
ማዳኔ በቅርብ ነው፤
ጽድቄም ፈጥኖ ይገለጣልና።
[2]ሰንበትን ሳያረክስ የሚያከብር፣
ክፉን ከማድረግ እጁን የሚሰበስብ፣
የሚገታ፣
እነዚህን የሚፈጽም ሰው የተባረከ ነው።"

[3]ወደ እግዚአብሔር የተጠጋ መጻተኛ፣
"እግዚአብሔር በእርግጥ ከሕዝቡ ይለየኛል"
አይበል፤
ጃንደረባም፣
"እኔ ደረቅ ዛፍ ነኝ" አይበል።

[4]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"ሰንበቶቼን ለሚያከብሩ ጃንደረቦች፣
ደስ የሚያሰኘኝን ለሚመርጡ፣
ቃል ኪዳኔን፣ ለሚጠብቁ
[5]በቤተ መቅደሴና በቅጥሮቼ ውስጥ፣
ከወንዶችና ከሴቶች ልጆች የበለጠ፣
መታሰቢያና ስም እሰጣቸዋለሁ፤
ለዘላለም፣
የማይጠፋ ስም እሰጣቸዋለሁ።
[6]እርሱን ለማገልገል፣
ራሳቸውን ከእግዚአብሔር ጋር ያቈራኙ
መጻተኞች፣
የእግዚአብሔርን ስም በመውደድ፣
እርሱንም በማምለክ፣
ሰንበትን ሳያረክሱ የሚያከብሩትን ሁሉ፣
ቃል ኪዳኔንም የሚጠብቁትን፣
[7]ወደ ተቀደሰው ተራራዬ አመጣቸዋለሁ፤
በጸሎት ቤቴም ውስጥ ደስ አሰኛቸዋለሁ።
የሚቃጠል መሥዋዕታቸውንና ሌሎች
መሥዋዕቶቻቸውን፣
በመሠዊያዬ ቢሠዉ እቀበላቸዋለሁ፤
ቤቴ፣ ለሕዝቦች ሁሉ
የጸሎት ቤት ተብሎ ይጠራልና።"
[8]የተበተኑትን እስራኤል የሚሰበስብ፣
ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"ከተሰበሰቡት በተጨማሪ፣
ሌሎችን እንደ ገና እሰበስባለሁ።"

ኢዮ11፥8፤ መዝ103፥11፤ ኢሳ40፥13-14
55፥10 ዘፍ47፥23፤ ዘሌ25፥19፤ ኢዮ14፥9፤ መዝ67፥6፤ ኢሳ30፥23፤ 2ቆሮ9፥10
55፥11 ዘዳ32፥2፤ ምሳ19፥21፤ ኢሳ40፥8፤ 44፥26፤45፥23፤ ሕዝ12፥25፤ ማቴ5፥18፤ ዮሐ1፥1፤ ዕብ4፥12
55፥12 1ዜና16፥33፤ መዝ65፥12-13፤ 96፥12-13፤98፥4:8፤ ኢሳ35፥2፤54፥10:13
55፥13 ዘኍ33፥55፤ መዝ102፥12፤ኢሳ5፥6፤ 41፥19፤63፥12፤ ኤር32፥20፤33፥9
56፥1 መዝ11፥7፤ 85፥9፤ኢሳ1፥17፤ 26፥8፤ኤር22፥3፤ 23፥6፤ዳን9፥24
56፥2 ዘፀ20፥8:10፤ መዝ119፥2
56፥3 ዘፀ12፥43፤ ዘሌ21፥20፤ዘዳ23፥3፤ 1ነገ8፥41፤ኢሳ11፥10፤ ኤር38፥7፤ዘካ8፥20-23፤ ሐሥ8፥27
56፥4 ዘፀ31፥13፤ ኤር38፥7
56፥5 ዘኍ32፥42፤ 1ሳሙ15፥12፤ ኢሳ26፥1፤43፥7፤ 48፥19፤55፥13፤ 60፥18
56፥6 ቍ2:4፤ ዘፀ12፥43፤1ነገ8፥41፤ 1ዜና22፥2፤ኢሳ60፥7:10፤61፥5፤ሚል1፥11
56፥7 ኢሳ2፥2፤ 19፥21፤ሕዝ20፥40፤ ማቴ21፥13፤ ማር11፥17፤ ሉቃ19፥46፤ ሮሜ12፥1፤ፊል4፥18፤ዕብ13፥15
56፥8 ዘዳ30፥4፤ኢሳ11፥9፤ 11፥12፤60፥3-11፤ሕዝ34፥12፤ዮሐ10፥16

55፥11 *ቃሌ፤* በተለይ በቍ3:5:12 ላይ ያሉትን የተስፋ ቃሎች ማመልከቱ ነው። ቃሉ እንደ መልእክተኛ ሆኖ በ9፥8፤ በመዝ107፥20 ላይ ይታያል፤ ከዮሐ1፥1 ጋር ያነጻጽሩ። *የተላከበትንም ዐላማ፤* 46፥10-11 እና ማብ ይመ፤ ከ40፥8፤ ዕብ4፥12 ጋር ያነጻጽሩ።

55፥12 *በደስታ ትወጣላችሁ፤* ከባቢሎን ሲወጡ በብዙ ድጋፍና ምርኮ እንደሚወጡ ለማመልከት ነው (35፥10 እና ማብ፤ 52፥9-12 እና ማብ ይመ)። *ተራሮችና... በእልልታ ይዘምራሉ፤* 44፥23 እና ማብ ይመ። *ያጨበጭባሉ፤* ዘይቤያዊ አገላለጽ (ከ1ዜና16፥33፤ መዝ98፥8፤114፥3-6 ጋር ያነጻጽሩ)።

55፥13 *በእሾኽ ... የጥድ ... በኵርንችት ... ባርሰነት፤* ይህ ኢሳይያስ ከዚህ በፊት ስለ ምድረ በዳነት ለተናገረው ትንቢት ተቃራኒ ነው (5፥6፤32፥13)፤ ስለ ዛፎቹ ምንነት 35፥2፤ 41፥19 እና ማብ ይመ። *የእግዚአብሔር መታሰቢያ፤* እስራኤልን ከግብፅ ባወጣ ጊዜ እግዚአብሔር የነበረውን ዐይነት ዝና የሚያንጸባርቅ መታሰቢያ ነው (63፥12:14 ይመ)። *የዘላለም ምልክት፤* የእግዚአብሔር ታዳጊነት ፍጹም የሚረሳ አይደለም፤ ከ19፥20፤ 56፥5 ጋር ያነጻጽሩ።

56፥1 *ማዳኔ ... ጽድቄም፤* 45፥8፤ 46፥13፤ 51፥5 እና ማብ ይመ።

56፥2 *ሰንበትን ... የሚያከብር፤* ቍ4:6 ይመ። እግዚአብሔር እስራኤላውያንን ከግብፅ ካወጣቸው በኋላ ሰንበትን እንዲያከብሩ እንዳዘዛቸውና (ዘፀ20፥8-11) ከሙሴም ጋር ለተደረገው ቃል ኪዳን ምልክት እንደ ሆነ (ዘፀ31፥13-17)፣ አሁንም እግዚአብሔር ሕዝቡን እንደ ገና መታደጉ (55፥12) ሙሉ በሙሉ ለእርሱ እንዲታዘዙለት ዕድል ሰጣቸው፤ መታዘዛቸውም፣ "ሰንበትን በማክበር" ተጠቃሎአል (58፥13፤ 66፥23፤ ኤር17፥21-27፤ ሕዝ20፥20-21 ይመ)።

56፥3 *መጻተኛ፤* ቍ6 ይመ። በእስራኤላውያን መካከል ለመኖር የመጡ አሕዛብ ቢያንስ ሦስት፣ አራት ትውልድ እስኪያልፍ ድረስ በሥርዐተ አምልኰው እንዲካፈሉ አይፈቀድላቸውም ነበር (ዘፀ12፥43፤ ዘዳ23፥3:7-8 ይመ)፤ ይሁን እንጂ የእግዚአብሔር አገልጋይ የመሲሑ ሥራ ይህን ሁኔታ ለውጦታል(49፥19-20፤ 54፥17 60፥10 እና ማብ ይመ)፤ ከ14፥1 ጋር ያነጻጽሩ። *ጃንደረባም፤* ቍ4 ይመ፤ ጃንደረባዎች በእግዚአብሔር ጉባኤ መካከል እንዲገኙ አይፈቀድላቸውም ነበር (ዘዳ23፥1)፤ ይሁን እንጂ የእግዚአብሔር ሕዝብ ወገን ይሆናሉ (ሐሥ8፥27:38-40 ይመ)።

56፥4:6 *ለሚጠብቁ፤* እንደ ግዝረት ሁሉ (ዘፍ17፥11)፣ ሰንበትን ማክበርም የቃል ኪዳን ምልክት ነበረ (ዘጸ31፥13-17፤ ሕዝ20፥12:20 ይመ)።

56፥5 *መታሰቢያና፤* አቤሴሎም በሕይወት ያሉ ልጆች ስላልነበሩት፣ ሐውልት ሠርቶ ነበር (2ሳሙ18፥18)። "*መታሰቢያና ስም*"፤ በዕብራይስጥ አንድ ዐይነት ቃል ነው 55፥13 ይመ። *የማይጠፋ፤* አንዳንድ ጊዜ ስምን ከትውልድ እስከ ትውልድ ለማስተላለፍ ሲባል የሚነገር ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው።

56፥6 *ለማገልገል፤* ከ60፥7:10 ጋር ያነጻጽሩ።

56፥7 *ወደ ተቀደሰው ተራራዬ፤* 2፥2-4 እና ማብ ይመ። *መሥዋዕቶቻቸውን በመሠዊያዬ፤* ከ60፥7 ጋር ያነጻጽሩ፤ ከ1፥11-13 ጋር ያስተያዩ። *ለሕዝቦች ሁሉ የጸሎት ቤት፤* ንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደሱ በተመረቀ ጊዜ ባቀረበው ጸሎት ይህን አስቀድሞ ተናግሮታል (1ነገ8፥41-43)።

56፥8 *የተበተኑትን ... የሚሰበስብ፤* 11፥11-12 እና ማብ ይመ። *ሌሎችን ... እሰበስባለሁ፤* አሕዛብንም ጭምር ማለት ነው (ቍ3 እና ማብ ይመ፤ ከዮሐ10፥16 ጋር ያነጻጽሩ)።

### በክፉዎች ላይ የእግዚአብሔር ወቀሳ

[9]እናንት የምድር አራዊት ሁሉ ኑ፤
እናንት የዱር አራዊት ሁሉ ኑና በጥርሳችሁ በጫጭቁ።
[10]የእስራኤል ጠባቂዎች ዕውሮች ናቸው፤
ዕውቀት የላቸውም፤
ሁሉም ድምፅ የለሽ ውሾች ናቸው፤
መጮኽ አይችሉም፤
ተጋድመው ያልማሉ፤
እንቅልፋሞች ናቸው።
[11]እጅግ ሲበዛ ሆዳም ውሾች ናቸው፤
ጠገብሁን አያውቁም፤
የማያስተውሉ እረኞች ናቸው፤
ሁሉም በየራሳቸው መንገድ ሄዱ፤
እያንዳንዳቸውም የግል ጥቅማቸውን ፈለጉ።
[12]እርስ በርሳቸውም፣ "ኑና የወይን ጠጅ እንገባበዝ፤
እስክንሰክር እንጠጣ፤
ነገም ያው እንደ ዛሬ፣
ምናልባትም የተሻለ ቀን ይሆንልናል"
ይባባላሉ።

**57** ጻድቅ ይሞታል፤
ይህን ግን ማንም ልብ አይልም፤
ለእግዚአብሔር ያደሩ ሰዎች ይወሰዳሉ፤
ጻድቃን ከክፉ ይድኑ ዘንድ፣
መወሰዳቸውን፣
ማንም አያስተውልም።
[2]በቅንነት የሚሄዱ፣
ሰላም ይሆንላቸዋል፤
መኝታቸው ላይ ያርፋሉ።
[3]"እናንት የአስማተኛዪቱ ልጆች ግን፣
እናንት የአመንዝራውና የጋለሞታዪቱ ዘር፤ እናንት፣ ወዲህ ኑ፤
[4]የምትሣለቁት በማን ላይ ነው?
የምታሽሟጥጡት ማንን ነው?
ምላሳችሁንስ አውጥታችሁ የምታሾፉት በማን ላይ ነው?
እናንት የዐመፀኞች ልጆች፣
የሐሰተኞች ዘር አይደላችሁምን?
[5]በባሉጥ ዛፎች መካከል፣
ቅጠሉ በተንዠረገገ ዛፍ ሥር በዝሙት የምትቃጠሉ፣
በሸለቆዎች፣
በዐለት ስንጣቂዎችም ውስጥ ልጆቻችሁን የምትሠዉ አይደላችሁምን?
[6]በሸለቆው በሚገኙት ለስላሳ ድንጋዮች ውስጥ ያሉት ጣዖቶች የአንቺ ናቸው፤
እነርሱም ዕጣ ፈንታዎችሽ ናቸው፤
እርግጥ ነው፣ በእነርሱ ላይ የመጠጥ ቍርባን አፍስሰሻል፤
የእህል ቍርባንም አቅርበሻል፤
ታዲያ፣ ስለ እነዚህ ነገሮች ዝም እላለሁን?
[7]ዐልጋሽን ከፍ ባለውና በረጅሙ ኰረብታ ላይ አነጠፍሽ፤
በዚያም መሥዋዕትሽን ልታቀርቢ ወጣሽ።
[8]ከመዝጊያሽና ከመቃንሽ ጀርባ፣
የጣዖት ምስሎችሽን ሰቀልሽ፤
እኔን ትተሽ መኝታሽን ገላለጥሽ፤
በላይም ወጥተሽ በጣም ገለጥሽው፤
መኝታቸውን ከወደድሽላቸው ጋር ስምምነት አደረግሽ፤
ዕርቃናቸውንም አየሽ።
[9]የወይራ ዘይት ይዘሽ፣
ሽቶ በላዩ ጨምረሽ ወደ ሞሎክ* ሄድሽ፤
መልእክተኞችሽን° ወደ ሩቅ አገር ላክሽ፤
እስከ ራሱ እስከ ሲኦልም ዘለቅሽ።
[10]በመንገድ ብዛት ደከምሽ፤
ነገር ግን 'ተስፋ የለውም' አላልሽም፤
የጕልበት መታደስ አገኘሽ፤
ስለዚህም አልዛልሽም።

56፥9 ኢሳ18፥6፤ ኤር12፥9፤ሕዝ34፥5፡8፤39፥17-20
56፥10 ኢሳ52፥8፤ 62፥6፤ኤር2፥8፤6፥17፤ 10፥21፤14፥13-14፤ 31፥6፤ሕዝ3፥17፤ 33፥7፤ናሆ3፥18
56፥11 ኢሳ1፥3፤ 53፥6፤57፥17፤ ኤር6፥13፤8፥10፤ 22፥17፤23፥1፤ ሕዝ13፥19፤34፥2፤ ሆሴ4፥7-8፤ሚክ3፥11
56፥12 ዘሌ10፥9፤ መዝ10፥6፤ምሳ23፥20፤ ኢሳ22፥13፤ ሉቃ12፥18-19
57፥1 2ነገ22፥20፤ መዝ12፥1፤ ኢሳ42፥25፤ሕዝ21፥3
57፥2 ኢሳ26፥7፤ ዳን12፥13
57፥3 ቍ7-8፤ ዘፀ22፥18፤ኢሳ1፥21፤ ኤር2፥20፤ሚል3፥5፤ ማቴ16፥4፤ያዕ4፥4
57፥4 ኢሳ1፥2
57፥5 ዘዳ12፥2፤ 18፥10፤ዘሌ18፥21፤ 2ነገ16፥4፤ መዝ106፥37-38፤ ኢሳ1፥29፤ሕዝ16፥20
57፥6 2ነገ17፥10፤ ኤር3፥9፤5፥9፡29፤ 7፥18፤9፥9፤19፥13፤ 44፥18፤ዕን2፥19
57፥7 ኢሳ65፥7፤ ኤር3፥6፤13፥27፤ ሕዝ6፥3፡13፤16፥16፤ 20፥27-28፡29
57፥8 ሕዝ16፥15፡ 26፡36፤23፥7፡18
57፥9 ዘሌ18፥21፤ 1ነገ11፥5፤መሐ4፥10፤ ኢሳ8፥19፤ ሕዝ23፥16፡40
57፥10 1ሳሙ2፥4፤ ኢሳ47፥13፤ኤር2፥25፤ 18፥12፤ሚል3፥14

*9 ወይም ወደ ንጉሡ
°9 ወይም፣ ጣዖቶችሽን

*56፥9-59፥15፤* በዚህ ክፍል የተጠቀሱ ብዙ ጥቅሶች ለባቢሎን ምርኮ ዘመን ወይም ከዚያ በፊት ላሉ ሁኔታዎች ሊጠቀሱ የሚችሉ ናቸው።

56፥9 *የምድር አራዊት፤* የውጭ ወራሪዎችን ለማመልከት ነው (18፥6 እና ማብ ይመ)።

56፥10 *ጠባቂዎች፤* ነቢያትን ለማመልከት ነው (ዕን2፥1 ይመ)። *ዕውሮች ... እንቅልፋሞች፤* ከ29፥9-10 ጋር ያነጻጽሩ። *ድምፅ የለሽ ውሾች፤* በጎችን የሚጠብቁ ውሾችን ለማመልከት ነው (ከኢዮ30፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

56፥11 *ሆዳም፤* በጎችን በጫጭቀው ይበላሉ፤ ሕዝ34፥3 ይመ። *እረኞች፤* መሪዎችንም ጭምር ማለት ነው፤ ሕዝ34፥1-6 ይመ።

56፥12 *የወይን ጠጅ ... እስክንሰክር፤* በ28፥7 ላይ ከተገለጸው ከነቢያትና ከካህናት ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ። *ነገም ... የተሻለ ቀን፤* በሉቃ12፥19 ላይ ከተጠቀሰው ከሰነፉ ሀብታም አነጋገር ጋር ያነጻጽሩ።

57፥1 *ከክፉ ይድኑ ዘንድ፤* ነቢዪቱ ሕልዳና ጻድቁ ንጉሥ ኢዮስያስ ጥፋት ከመምጣቱ በፊት የሰላም ሞት እንደሚሞት ተናገረች (2ነገ22፥19-20)።

57፥2 *ሰላም፤* ከቍ21 ጋር ያነጻጽሩ። *ዕረፍት ያገኛሉ፤* ጳውሎስ በፊል1፥21፡23 ላይ ከተናገረው ቃል ጋር ያነጻጽሩ።

57፥3 *የአስማተኛዪቱ፤* የድግምት ወይም የጥንቈላ ሥራ የምትሠራ ማለት ነው (3፥2፤ 47፥12፤ ዘዳ18፥10 ይመ)። *የአመንዝራውና የጋለሞታዪቱ፤* መንፈሳዊ ምንዝርናን ለመግለጽ ነው (ቍ5-8 ይመ)።

57፥4 *የምትሣለቁት ... የምታሽሟጥጡት፤* በ28፥9፡14 ላይ ሕዝቡ በኢሳይያስ እንደ ተሣለቁበት ተጽፎአል።

57፥5 *በወርካ ዛፎች፤* አሕዛብ ለአምልኮ ጣዖት ተግባር የሚገለገሉባቸው ዛፎች ናቸው (1፥29 እና ማብ ይመ)። *በተንዠረገገ ዛፍ፤* በ1ነገ14፥23 ላይ እንደ ተገለጸው በኰረብታ ላይ ካሉ የጣዖት አምልኮ ስፍራዎች ጋር የተያያዘ ነው። ከኤር2፥20፤ 3፥13 ጋር ያነጻጽሩ። *ልጆቻችሁን የምትሠዉ፤* አብዛኛውን ጊዜ ከሞሎክ አምልኮ ጋር የተያያዘ ነው (ከቍ9 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ30፥33 ማብ ይመ)፤ ከበኣል አምልኮም ጋር ይያያዛል (ኤር19፥5)። በመዝ106፥37-38 ልጆች ለጣዖትና ለአጋንንት እንደሚሠዉ ተገልጾአል።

57፥6 *በሸለቆው፤* ከኢየሩሳሌም በስተ ደቡብ ምዕራብ ያለውን ሞሎክ የሚመለክበትን የሄኖም ሸለቆ የሚመለከት ሊሆን ይችላል። *የመጠጥ ቍርባን፤* የሚፈሱ ቍርባኖችን ለጣዖት አምልኮ ማቅረብ የተለመደ ነበር።

57፥7 *ከፍ ባለውና በረጅሙ ኰረብታ፤* በ"ጕብታዎች" ወይም በ"ተራራ ላይ ማምለኪያዎች" ማለት ነው (ኤር3፥6፤ ሕዝ16፥16፤ 22፥9 ይመ)።

57፥8 *ከወደድሽላቸው፤* የጣዖት አማልክትን ወይም ምስሎቻቸውን ያመለክታል።

57፥9 *የወይራ ዘይት፤* ለሽቱ ቅባትነት ያገለግላል፤ ማሕ 4፥10 ይመ። *ሞሎክ፤* የአሞናውያን ዋና ጣዖት ነው (ቍ5 እና ማብ፤ 1ነገ11፥7 ይመ)። *እስከ ሲኦልም፤* ከ8፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

57፥10 *ተስፋ የለውም፤* ከራሳቸው ሐሳብም ሆነ ከሚያመልኳቸው ጣዖቶች ዘወር ማለት አይገባም የሚሉትን የሚገልጽ ሽሙጥ ዘይቤያዊ አባባል ነው። *የጕልበት መታደስ፤* ከ40፥30-31 ጋር ያስተያዩ።

[11]“እኔን የዋሸሽኝ፤
  ማንን ፈርተሽ፣ ማንንስ ሠግተሽ ነው?
እኔን ያላስታወስሽው፣
  ይህንንም በልብሽ ያላኖርሽው፣
እኔን ያልፈራሽው፣
  ዝም ስላልሁ አይደለምን?
[12]ጽድቅሽንና ሥራሽን አጋልጣለሁ፤
  እነርሱም አይጠቅሙሽም።
[13]ለርዳታ በምትጮኺበት ጊዜ፣
  የሰበሰብሻቸው ጣዖቶች እስቲ ያድኑሽ!
ነፋስ ጠራርጎ ይወስዳቸዋል፤
  ሽውሽውታም ይበትናቸዋል።
እኔን መጠጊያው ያደረገ ሰው ግን፣
  ምድሪቱን ይወርሳል፤
የተቀደሰ ተራራዬንም ገንዘቡ ያደርገዋል።”

## ልባቸው ለተሰበረ መጽናናት

[14]እንዲህ ይባላል፤
  “አብጁ፤ አብጁ፤ መንገድ አዘጋጁ፤
  ከሕዝቤ መንገድ ዕንቅፋት አስወግዱ።”
[15]ከፍ ከፍ ያለውና ልዕልና ያለው እርሱ፣
  ስሙም ቅዱስ የሆነው፣ ለዘላለም የሚኖረው
    እንዲህ ይላል፤
“የተዋረዱትን መንፈሳቸውን ለማነሣሣት፣
  የተሰበረ ልብ ያላቸውን ለማነቃቃት፣
ከፍ ባለውና በቅዱሱ ስፍራ እኖራለሁ፤
  የተሰበረ ልብ ካለውና በመንፈሱ ከተዋረደው
    ጋር እሆናለሁ።
[16]የሰው መንፈስ በፊቴ እንዳይዝል፣
  የፈጠርሁትም ሰው እስትንፋስ እንዳይቆም፣
ለዘላለም አልወቅስም፤
  ሁልጊዜም አልቈጣም።
[17]ኀጢአት ስለ ሞላበት ስግብግብነቱ
    ተቈጣሁት፤
  ቀጣሁት፤ ፊቴንም በቍጣ ከእርሱ ሸሸግሁ፤
  ያም ሆኖ በገዛ መንገዱ ገፋበት።
[18]መንገዶቹን አይቻለሁ፤ ቢሆንም እፈውሰዋለሁ፤
  እመራዋለሁ፤ ለእርሱና ስለ እርሱ ለሚያለቅሱትም መጽናናትን እመልሳለሁ፤
[19] በእስራኤል አልቃሾች ከንፈር ላይ ምስጋና
    እፈጥራለሁ።
  በቅርብና በሩቅ ላሉት ሰላም፣ ሰላም ይሁን፤
  እኔ እፈውሳቸዋለሁ” ይላል እግዚአብሔር።
[20]ክፉዎች ግን ማዕበሉ ጭቃና ጕድፍ
    እንደሚያወጣ፣
  ጸጥ ማለት እንደማይችል፣
  እንደሚናወጥ ባሕር ናቸው።
[21]አምላኬ፣ “ለክፉዎች ሰላም የላቸውም”
    ይላል።

## እውነተኛ ጾም

**58** “በኀይል ጩኽ፤ ምንም አታስቀር፤
  ድምፅህን እንደ መለከት አሰማ፤
    ለሕዝቤ ዐመፃቸውን፣
  ለያዕቆብም ቤት ኀጢአታቸውን ተናገር።
[2]ዕለት በዕለት ይፈልጉኛል፤
  መንገዴን ለማወቅ የሚጓጉ ይመስላሉ፤
ትክክለኛውን ነገር እንደሚያደርግ፣
  የአምላኩንም ትእዛዝ እንዳልተወ ሕዝብ ሁሉ፣
ተገቢ የሆነ ፍትሕ ይለምኑኛል፤
  እግዚአብሔር ወደ እነርሱ እንዲቀርብ
    የሚወዱም ይመስላሉ።
[3]‘አንተ ካልተቀበልኸው፣
  ስለ ምን ብለን ጾምን?
አንተ ከጕዳይ ካልቈጠርኸው፣
  ስለምን ራሳችንን አዋረድን?’ ይላሉ።

“ሆኖም በጾማችሁ ቀን የልባችሁን
    ታደርጋላችሁ፤
  ሠራተኞቻችሁንም ትበዘብዛላችሁ።

57፥11 2ነገ1፥15፤ አስ4፥14፤ምሳ29፥25፤ መዝ50፥21፤83፥1፤ ኢሳ7፥2፤ 17፥10፤ 42፥23፤ ኤር2፥32፤ 3፥21፤13፥25፤18፥15፤ ሕዝ22፥12
57፥12 ኢሳ29፥15፤ 58፥1፤59፥6፡12፤ 65፥7፤66፥18፤ ሕዝ16፥2፤ ሚክ3፥2-4፡8
57፥13 መሳ10፥14፤ መዝ37፥9፤118፥8፤ ኢሳ2፥2-3፤40፥7፡ 24፤56፥7፤65፥9-11፤ ኤር22፥20፤30፥15
57፥14 ኢሳ11፥16፤ 62፥10፤18፥15
57፥15 ዘዳ33፥27፤ 2ነገ22፥19፤ኢዮ5፥18፤ 16፥19፤መዝ34፥18፤ 51፥17፤90፥2፤147፥3፤ ኢሳ52፥13፤66፥2፤ ሚክ6፥8፤ማቴ5፥3፤ 23፥12
57፥16 ዘፍ2፥7፤ መዝ50፥21፤103፥9፤ ኢሳ3፥13-14፤54፥9፤ ዘካ12፥1
57፥17 ኢሳ1፥4፡15፤ 30፥15፤53፥6፤56፥11፤ 66፥3፤ኤር8፥10
57፥18 ዘዳ32፥39፤ 2ዜና7፥14፤መዝ48፥14፤ ኢሳ30፥26፤42፥16፤ 48፥17፤49፥13፤ 61፥1-3
57፥19 ኢሳ2፥4፤ 6፥7፤26፥3፡12፤ 32፥17፤51፥16፤ 59፥21፤ሉቃ2፥14፤ ሐሥ2፥39፤ ዕብ13፥15
57፥20 ዘፍ49፥4፤ ኢዮ18፥5-21፤ መዝ69፥14፤ ኤፌ4፥14፤ይሁ1፥13
57፥21 ኢሳ26፥3፤ 48፥22፤59፥8፤ ሕዝ13፥16

58፥1 ዘፀ20፥18፤ኢሳ24፥20፤40፥6፤48፥8፤57፥12፤ሕዝ3፥17
58፥2 ዘዳ32፥15፤መዝ119፥87፤ኢሳ29፥13፤48፥1፤ቲቶ1፥16፤ ያዕ4፥8 58፥3 ዘፀ10፥3፤ዘሌ16፥29፤2ዜና6፥37፤ኢሳ22፥13፤ ኤር44፥10፤ዘካ7፥5-6፤ሚል3፥14

57፥11 *ማንን ፈርተሽ ማንንስ ሰግተሽ፤* ሰዎችን ይፈሩ ነበር (51፥12 ይመ)። *እኔን ያላስታወስሽው፤* 51፥13 ይመ። *ዝም ስላልሁ፤* እግዚአብሔር የፍርድ ርምጃ አልወሰደም ነበር (42፥14 እና ማብ ይመ)።

57፥12 *ጽድቅሽንና፤* 58፥2-3፤64፥6 ይመ።

57፥13 *ጣዖቶች … ያድኑሽ፤* 44፥17 እና ማብ ይመ። *ነፋስ ጠራርጎ ይወስዳቸዋል፤ ሽውሽውታም ይበትናቸዋል፤* ጣዖቶች ከሰው የሚበልጥ ጥንካሬ የላቸውም። *እኔን መጠጊያው ያደረገ፤* 25፥4 ይመ። *ምድሪቱን ይወርሳል፤* 49፥8 እና ማብ ይመ። *የተቀደሰ ተራራዬንም፤* 2፥2-4 እና ማብ ይመ።

57፥14 *አብጁ፤ አብጁ መንገድ፤* የ40፥1 ማብ ይመ። *መንገድ … አዘጋጁ፤* 40፥3 እና ማብ ይመ።

57፥15 *ከፍ ከፍ ያለውና ልዕልና ያለው፤* 6፥1፤ 52፥13 እና ማብ ይመ፤ ከ33፥5 ጋር ያነጻጽሩ። *የተሰበረ ልብ፤* ልባቸው የሚንቀጠቀጥ ለማለት ነው (53፥5 ይመ)።

57፥16 *ለዘላለም አልወቅስም፤* በተደጋጋሚ እስራኤልን በፍርድ አደባባይ አቅርቦአት ነበርና ነው (3፥13-14 ይመ)። *አልቈጣም፤* 54፥9 እና ማብ፤ ኤር3፥12 ይመ።

57፥17 *ፊቴንም በቍጣ ከእርሱ ሸሸግሁ፤* 54፥8፤1፥15 እና ማብ ይመ።

57፥18 *እፈውሰዋለሁ፤* ቍ19፤ 6፥10፤ 30፥26፤ ኤር3፥22 ይመ። እግዚአብሔር ለሕዝቡ ይቅርታ አድርጎ፣ ወደ አገሩ ይመልሰዋል። *እመራዋለሁ፤* 49፥13 እና ማብ ይመ።

57፥19 *አልቃሾች፤* በኢየሩሳሌም ላይ ከወረደው ፍርድ የተነሣ የሚያለቅሱትን ማለት ነው (66፥10 ይመ)። *ሰላም፣ ሰላም፤* ከኤር6፥13-14፤ 8፥10-11 ያነጻጽሩ። *በሩቅ ላሉት፤* አሕዛብን ወይም የተማረኩትን አይሁድ ለማመልከት ይሆናል፤ ጳውሎስ ለኤፌሶን ሰዎች (ኤፌ 2፥17) የጻፈው ምናልባት ይህ ትዝ ብሎት ሳይሆን አይቀርም።

57፥20 *ጸጥ ማለት እንደማይችል፤* ከቍ2 ጋር ያነጻጽሩ። *እንደሚናወጥ ባሕር፤* ኤር49፥23 ይመ።

*57፥21፤* 39፥8፤ 48፥22 እና ማብ ይመ።

58፥1 *ድምፅህን እንደ መለከት፤* ኀይለኛው የእግዚአብሔር ድምፅ በሲና ተራራ ላይ ከተነፋው የመለከት ድምፅ ጋር ተነጻጽሮአል (ዘፀ19፥19፤ 20፥18-19 ይመ)። *ዐመፃቸውን፤* 1፥2 እና ማብ ይመ። *ኀጢአታቸውን፤* 1፥4፤59፥12-13 ይመ።

58፥2 *ይፈልጉኛል፤* 55፥6 እና ማብ ይመ። በ1፥11 ላይ ከተጠቀሱት በተከታታይ ከቀረቡት መሥዋዕቶች ጋር ያነጻጽሩ። *እግዚአብሔር ወደ እነርሱ እንዲቀርብ፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ግብዝነት በ29፥13 ላይ ተገልጾአል (የዚያኑ ማብ ይመ)።

58፥3 *ጾምን … በጾማችሁ፤* ቍ6 ይመ። በተሠራ ኀጢአት ንስሓ የመግባትና ራስን የመካድ ጊዜ ነው። ኢየሩሳሌም ከወደቀች በኋላ፣ የጾም ቀኖች ቍጥር ጨምሮአል (ዘሌ16፥29፤ ዘካ7፥5 ይመ)። *ራሳችንን አዋረድን፤* ከ2ዜና7፥14፤1ነገ21፥29 ጋር ያነጻጽሩ። *አንተ ከጕዳይ ካልቈጠርኸው፤* በሚል 3፥4 ላይ ከተገለጸው ተመሳሳይ ሐሳብ ጋር ይህን ያስተያዩ፤ ከሉቃ18፥12 ጋር ያነጻጽሩ። *ሠራተኞቻችሁንም ትበዘብዛላችሁ፤* 3፥14-15፤ 10፥2 ይመ።

4ጾማችሁ በጥልና በክርክር፣
  በግፍ ጡጫና በመደባደብ ይፈጸማል፤
ከእንግዲህ ዛሬ እንደምትጾሙት ጾማችሁ፣
  ድምፃችሁ ወደ ላይ እንደሚሰማም ተስፋ
    አታድርጉ።
5እኔ የመረጥሁት ጾም እንዲህ ዐይነቱን ነውን?
  ሰውስ ራሱን የሚያዋርደው በእንዲህ ያለው
    ቀን ብቻ ነውን?
እንደ ደንገል ራስን ዝቅ ማድረግ ነውን?
  ወይስ ማቅ ለብሶ በዐመድ ላይ መንከባለል
    ነውን?
ታዲያ ጾም ብለህ የምትጠራው ይህን ነውን?
  *እግዚአብሔርስ* የሚቀበለው እንዲህ ያለውን
    ቀን ነውን?

6"እንግዲህ እኔ የመረጥሁት ጾም፣
  የጭቈናን ሰንሰለት እንድትበጥሱ፣
የቀንበርን ገመድ እንድትፈቱ፣
  የተጨቈኑትን ነጻ እንድታወጡ፣
  ቀንበርን ሁሉ እንድትሰብሩ አይደለምን?
7ምግብህን ለተራበ እንድታካፍለው፣
  ተንከራታቹን ድኻ ወደ ቤትህ
    እንድታስገባው፣
የተራቈተውን ስታይ እንድታለብሰው፣
  የሥጋ ዘመድህንም ፊት እንዳትነሣው
    አይደለምን?
8ይህ ከሆነ ብርሃንህ እንደ ንጋት ጮራ
    ይፈነጥቃል፤
  ፈውስህ ፈጥኖ ይደርሳል፤
ጽድቅህ[+] ቀድሞህ ይሄዳል፤
  የ*እግዚአብሔር* ክብር ደጀን ይሆንልሃል።
9የዚያን ጊዜ ትጣራለህ፤
  *እግዚአብሔርም* ይመልስልሃል፤
ለርዳታ ትጮኻለህ፤ እርሱም፣ 'አለሁልህ'
    ይልሃል።
  "የጭቈና ቀንበር፣
  የክፋትን ንግግርና ጣት መቀሰርን ከአንተ
    ብታርቅ፣
10ለተራበው ብትራራለት፣
  የተገፉት እንዲጠግቡ ብታደርግ፣
ብርሃንህ በጨለማ ያበራል፤
  ሌሊትህም እንደ ቀትር ፀሓይ ይሆናል።
11*እግዚአብሔር* ሁልጊዜ ይመራሃል፤
  ፀሓይ ባቃጠለው ምድር ፍላጎትህን ያሟላል፤
ዐጥንትህን ያበረታል፤
  በውሃ እንደ ረካ የአትክልት ቦታ፣
  እንደማይቋረጥም ምንጭ ትሆናለህ።
12ወገኖችህ የቀድሞ ፍርስራሾችን መልሰው
    ይሠራሉ፤
  የጥንቱንም መሠረት ያቆማሉ፤
አንተም፣ የተናዱ ቅጥሮችን አዳሽ፣
  ባለ አውራ መንገድ ከተሞችን ጠጋኝ
    ትባላለህ።

13"እግሮችህ ሰንበትን እንዳይሽሩ ብታሳርፍ፣
  በተቀደሰው ቀኔ የልብህን ባታደርግ፣
ሰንበትን ደስታ፣
  የ*እግዚአብሔርን* ቅዱስ ቀን የተከበረ ብለህ
    ብትጠራው፣
በገዛ መንገድህ ከመሄድ፣
  እንደ ፈቃድህ ከማድረግና ከከንቱ ንግግር
    ብትቈጠብ፣
14በዚያን ጊዜ *በእግዚአብሔር* ደስ ይልሃል፤
  በምድር ከፍታዎች ላይ እንድትጋልብ፣
የአባትህን የያዕቆብን ርስት ጠግበህ እንድትበላ
    አደርግሃለሁ"
  የ*እግዚአብሔር* አፍ ይህን ተናግሮአልና።

[+]8 *ወይም የአንተ ጻድቅ*

58፥4 1ሳሙ8፥18፤ 1ነገ21፥9-13፤ ኢሳ59፥2፡6፤ኤር6፥7፤ ሰቆ3፥44፤ሕዝ7፥11፤ 8፥18፤ሚክ3፥4፤ ሚል2፥16
58፥5 1ነገ21፥27፤ ኢዮ2፥8፤ኢሳ36፥6፤ ማቴ6፥16፤ዘካ7፥5
58፥6 ዘዳ14፥29፤ ነህ5፥10-11፤ኢሳ9፥4፤ 61፥1፤ኤር34፥9፤ ኢሌ2፥12-14፤ አሞ4፥1፤ሉቃ4፥19
58፥7 ዘፍ29፥14፤ ኢዮ22፥7፤ 31፥19-20፤ ኢሳ16፥4፤ሕዝ18፥16፤ ማቴ25፥36፤ ሉቃ3፥11፤10፥31-32፤ ዕብ13፥2
58፥8 ዘፀ14፥19፤ ኢዮ11፥17፤ኢሳ1፥5፤ 9፥2፤26፥2፤30፥26
58፥9 ኢዮ8፥6፤ መዝ12፥2፤50፥15፤ ምሳ6፥13፤ኢሳ30፥19፤ 59፥13፤ዳን9፥20፤ ዘካ10፥6
58፥10 ዘዳ15፥7-8፤ ኢዮ11፥17፤ኢሳ42፥16
58፥11 መዝ48፥14፤ 68፥6፤72፥16፤ 104፥28፤107፥9፤ ኢሳ35፥7፤42፥16፤ 48፥17፤መሐ4፥15፤ ዮሐ4፥14
58፥12 ነህ2፥17፤ ኢሳ44፥28፤49፥8
58፥13 ዘፀ20፥8፤ መዝ37፥4፤42፥4፤ 84፥2፡10፤ኢሳ59፥3
58፥14 ዘዳ32፥13፤ ኢዮ22፥26፤ መዝ105፥10-11፤ ኢሳ1፥20

58፥4 *ወደ ላይ እንዲሰማም፤* ግብዝነትን የተሞላ መንፈሳዊ ተግባር ለጸሎት ዕንቅፋት ነው (1፥15፤59፥2 ይመ)።

58፥5 *እንደ ደንገል፤* የደካማነትና የትሑት ሰብእና ምልክት ነው (42፥3 እና ማብ ይመ)። *ማቅ ለብሶ በዐመድ ላይ፤* ከ1ነገ21፥27፤ ዮና3፥5-8 ጋር ያነጻጽሩ። *የሚቀበለው፤* ብዙውን ጊዜ ከመሥዋዕት ጋር ተያይዞ የሚጠቀስ ቃል ነው (56፥7፤ 60፥7፤ ዘሌ1፥3 ይመ)።

58፥6 *የጭቈናን ሰንሰለት፤* ኢየሩሳሌም በተያዘች ጊዜ፣ ጌቶቻቸው መልሰው ሊይዟቸው ቢችሉም፣ ዕብራውያን ባሮች የዐዋጅ መብት አግኝተው ነጻ ወጥተው ነበር (ኤር34፥8-11)። *ቀንበር፤* ቍ9፤ 9፥4፤ 10፥27 ይመ፤ አሦራውያን በሕዝቡ ላይ ጭነውት የነበረው የጭቈና ቀንበር በዚያ ተጠቅሶአል። *የተጨቈኑትን፤* 1፥17 ይመ።

58፥7 *ምግብህን ለተራበ እንድታካፍለው፣ ተንከራታቹን ድኻ ወደ ቤትህ እንድታስገባው፣ የተራቈተውን ስታይ እንድታለብሰው፤* በሥጋዊ ዐይን የሚታይ እውነተኛ የጽድቅ ሥራ መገለጫ ኢዮ በ31፥17-20፤ ሕዝ በ18፥7፡16 እና ኢየሱስ ክርስቶስም በማቴ 25፥35-36 ራሱን ከተራቡና ከታረዙት ጋር ያመሳሰለበትን ይመ። *የሥጋ ዘመድህንም፤* ቅርብ ዘመድን የሚያመለክት ነው (ዘፍ37፥27)፤ ይሁን እንጂ 2ሳሙ5፥1 ይመ።

58፥8 *ብርሃንህ፤* ከእግዚአብሔር የሚገኘውን ደስታ፣ ብል ጽግናና ደኅንነት ለማመልከት ነው (9፥2፤ 60፥1-3 ይመ)። *ፈውስህ፤* 57፥18 እና ማብ ይመ። *ቀድሞህ ይሄዳል፤ ... ደጀን ይሆንሃል፤* 52፥12 እና ማብ ይመ። እግዚአብሔር ይጠብቃል፤ ይመራልም። *የእግዚአብሔር ክብር፤* ምናልባት በምድረ በዳ የተገለጠውን የደመናና የእሳት ዓምድ የሚያመለክት ነው (4፥5-6፤ ዘፀ 13፥21፤14፥20 እና ማብ ይመ)።

58፥9 *እግዚአብሔርም ይመልስልሃል፤* 30፥19 እና ማብ ይመ። *አለሁልህ፤* 65፥1 ይመ። *ጣት መቀሰርን፤* ሰውን የመናቅ ወይም የመንቀፍ መግለጫ ነው (ምሳ6፥13)። *የክፋትን ንግግር፤* ምሳ6፥12-14 ይመ።

58፥10 *ለተራበው ... የተገፉት፤* ቍ6-7 እና ማብ ይመ። *ብርሃንህ፤* ቍ8 እና ማብ ይመ።

58፥11 *ይመራሃል፤* 57፥18 እና ማብ ይመ። *ፍላጎትህን፤* ቁሳዊውንና መንፈሳዊውን ፍላጎት ማለት ነው (32፥2 እና ማብ ይመ)። *ፀሓይ ባቃጠለው ምድር፤* 35፥7፤49፥10 ይመ። *በውሃ እንደረካ የአትክልት ቦታ፤* በ1፥30 እንደ ተጠቀሰው ኢየሩሳሌም ውሃ ሳይኖራት ልዩ የአትክልት ቦታ ነበረች። *እንደማያቋርጥ ምንጭ፤* ይህን በዮሐ 4፥10፡14 ላይ ከተጠቀሰው፣ ኢየሱስ ክርስቶስ ከሚሰጠው፣ "የሕይወት ውሃ" ጋር ያነጻጽሩ።

58፥12 *የቀድሞ ፍርስራሾችን ... የጥንቱንም መሠረት፤* 44፥26፡28 እና ማብ፤ 61፥4፤ ሕዝ36፥10፤ አሞ9፥11፡14 ይመ። *የተናዱ ቅጥሮችን አዳሽ፤* በነህ2፥17 እንደ ተገለጸው የነህምያን ሥራ የሚያመለክት ነው።

58፥13 *ሰንበትን፤* 56፥2 እና ማብ ይመ። *በተቀደሰው ቀኔ፤* ለእግዚአብሔር የተለየ ቀንን ለማመልከት ነው (ዘፀ3፥5 እና ማብ ይመ)። *ደስታ፤* በእግዚአብሔርና (መዝ37፥4) በሕጉ ደስ ሊላቸው ይገባ ነበር (መዝ1፥2)። *በገዛ መንገድህ ከመሄድ፤* ምናልባት ሥጋዊ ተግባርን ለማከናወን መውጣት መውረድን የሚያመለክት ይሆናል (አሞ8፥5 ይመ)።

58፥14 *በእግዚአብሔር ደስ ይልሃል፤* 61፥10 ይመ። *ከፍታዎች ላይ እንድትጋልብ፤* ከዚህ የተነሣ ምድርን ትቈጣጠራለህ ማለት ነው። 33፥16 እና ማብ ይመ፤ ዕን3፥19 ይመ። *ርስት ጠግበህ እንድትበላ፤* በተስፋዪቱ ምድር የተትረፈረፈ ምግብ በመብላት ደስ መሰኘትን ያመለክታል (ዘዳ32፥13-14 ይመ)። *አፍ ይህን ተናግሮአልና፤* 40፥5 እና ማብ ይመ።

## ኀጢአት፣ ንስሓና መበገቴት

**59** እነሆ፤ *የእግዚአብሔር* እጅ ከማዳን
 አላጠረችም፤
 ጆሮውም መስማት አልተሳናትም
[2]ነገር ግን በደላችሁ ከአምላካችሁ ለይቶአችኋል፤
 ኀጢአታችሁ ፊቱን ከእናንተ ሰውሮታል፤
 በዚህም ምክንያት አይሰማም።
[3]እጆቻችሁ በደም፣
 ጣቶቻችሁ በበደል ተነክረዋል፤
ከንፈሮቻችሁ ሐሰትን ተናገሩ፤
 ምላሶቻችሁ ክፉ ነገርን አሰሙ።
[4]ፍትሕን የሚጠራ ማንም የለም፤
 ጕዳዩን በቅንነት የሚያቀርብ የለም፤
በከንቱ ነገር ታመኑ፤ ሐሰትን ተናገሩ፤
 ሁከትን ፀነሱ፤ ክፋትንም ወለዱ።
[5]የእባብ ዕንቍላል ታቀፉ፤
 የሸረሪት ድር አደሩ፤
ዕንቍላሎቻቸውን የሚበላ ሁሉ ይሞታል፤
 አንዱ በተሰበረ ጊዜም እፉኝት ይወጣል።
[6]ድሮቻቸው ልብስ አይሆኑም፤
 በሚሠሩትም ሰውነታቸውን መሸፈን
 አይችሉም፤
ሥራቸው ክፉ ነው፤
 እጃቸውም በዐመፅ ሥራ የተሞላ ነው።
[7]እግሮቻቸው ወደ ኀጢአት ይሮጣሉ፤
 ንጹሕ ደም ለማፍሰስ ይፈጥናሉ፤
የሚያስቡት ክፉ ሐሳብ ነው፤
 ማጥፋትና ማፈራረስም የመንገዳቸው
 ምልክት ነው።
[8]የሰላምን መንገድ አያውቁም፤
 በጕዳናቸውም ፍትሕ የለም፤
መንገዳቸውን ጠማማ አድርገውታል፤
 በዚያም የሚሄድ ሰላም አያገኝም።
[9]ስለዚህ ፍትሕ ከእኛ ርቆአል፤
 ጽድቅም ወደ እኛ አይመጣም፤
ብርሃንን ፈለግን፤ ነገር ግን ሁሉ ጨለማ ነው፤
 የብርሃንን ጸዳል ፈለግን፤ የምንሄደው ግን
 በድንግዝግዝታ ነው።
[10]በቅጥሩ ላይ እንደ ዕውር ተደናበርን፤
 አካሄዳችንም ዐይን እንደሌላቸው በዳበሳ ሆነ፤
ጀምበር በምትጠልቅበት ጊዜ እንደሚሆነው
 በእኩለ ቀን ተደናበርን፤
 በብርቱዎች መካከልም እንደ ሙታን ሆንን።
[11]ሁላችን እንደ ድቦች እንጮኻለን፤
 እንደ ርግቦችም በመቃተት እንጮኻለን፤
ፍትሕን ፈለግን፤ ግን አላገኘንም፤
 ትድግናን ፈለግን፤ ነገር ግን ከእኛ ርቆአል።
[12]በደላችን በፊትህ በዝቶአል፤
 ኀጢአታችን መስክሮብናል፤
በደላችን ከእኛ አልተለየም፤
 ዐመፀኝነታችንንም እናውቃለን።
[13]*በእግዚአብሔር* ላይ ዐምፀናል፤ ሐሰት
 ተናግረናል፤
 አምላካችንን ከመከተል ዘወር ብለናል፤
ዐመፃንና ግፍን አውርተናል፤
 ልባችን የፀነሰውን ውሸት ተናግረናል።
[14]ስለዚህ ፍትሕ ከእኛ ርቆአል፤
 ጽድቅም በሩቁ ቆሞአል፤
እውነት በመንገድ ላይ ተሰናክሎአል፤
 ቅንነትም መግባት አልቻለም።
[15]እውነት የትም ቦታ አይገኝም፤
 ከክፋት የሚርቅ ለጥቃት የተጋለጠ ነው።
*እግዚአብሔር* ተመለከተ፤
 ፍትሕ በመታጣቱም ዐዘነ።
[16]ማንም እንደሌለ አየ፤
 ወደ እርሱ የሚማልድ ባለመኖሩ ተገረመ፤

59፥1 ኢሳ30፥19፤ 41፥20፤50፥2፤58፥9፤ 65፥24
59፥2 መዝ18፥41፤ ኢሳ58፥4፤ኤር5፥25፤ 11፥11፤ሕዝ39፥23፤ ዮሐ9፥31
59፥3 2ነገ21፥16፤ መዝ7፥3፤ኢሳ1፥15፤ 3፥8፤ሕዝ22፥9
59፥4 ኢዮ4፥8፤ 15፥31፤ኢሳ5፥23፤ 29፥20፤44፥20፤ ያዕ1፥15
59፥5 ኢዮ8፥14፤ ኢሳ11፥8፤ማቴ3፥7
59፥6 መዝ55፥9፤ ምሳ4፥17፤ኢሳ28፥20፤ 58፥4
59፥7 2ነገ21፥16፤ ምሳ6፥17፤24፥2፤ ኢሳ26፥10፤ሚክ3፥10፤ ማር7፥21-22፤ ሮሜ3፥15-17
59፥8 መሳ5፥6፤ ኢሳ57፥21፤ሉቃ1፥79፤ ሮሜ3፥15-17
59፥9 ኢዮ19፥8፤ መዝ107፥14፤ ኢሳ5፥30፤8፥20፤ ሉቃ1፥79
59፥10 ዘዳ28፥29፤ ኢዮ3፥23፤ ኢሳ6፥9-10፤8፥15፤ 56፥10፤ሰቆ3፥6፤ 4፥14፤ሶፎ1፥17፤ ዮሐ11፥9-10
59፥11 ዘፍ8፥8፤ መዝ74፥19፤ኢሳ38፥14፤ ኤር48፥28፤ሕዝ7፥16፤ ናሆ2፥7
59፥12 ዘፍ4፥7፤ ዕዝ9፥6፤መዝ51፥3፤ ኢሳ3፥9፤57፥12፤ ኤር2፥19
59፥13 ዘኍ11፥20፤ መዝ12፥5፤ምሳ30፥9፤ ኢሳ3፥8፤5፥7፤44፥20፤ 46፥8፤48፥8፤ ማቴ10፥33፤ማር7፥21-22፤ ቲቶ1፥16
59፥14 ኢሳ1፥21፤29፥21፤ 48፥1፤ ኤር33፥16
59፥15 ኢሳ5፥7፤ኤር7፥28፤9፥5፤ዳን8፥12
59፥16 ኢሳ41፥28፤ 45፥8፡13፤46፥13፤ 51፥5፤53፥12

59፥1 *እጅ ... አላጠረችም፤* 51፥9 እና ማብ ይመ። *መስማት አልተሳናትም፤* 30፥19 እና ማብ ይመ።

59፥2 *ፊቱን ከእናንተ ሰውሮታል ... አይሰማም፤* 1፥15 እና ማብ ይመ።

59፥3-4 *ሐሰት፤* ቍ13፤ 28፥15፤ ሆሴ4፥2 ይመ።

59፥3 *በደም ... ተነክረዋል፤* ቍ7፤ 1፥15፡21፤ ሕዝ7፥23 ይመ።

59፥4 *ፍትሕን ... በቅንነት የሚያቀርብ፤* ድኾችና ረዳት የሌላቸው ተገቢ ፍርድ አያገኙም ነበር (ቍ14፤ 1፥17-23፤ 5፥7፡23 ይመ)። *ፀነሱ፤ ... ክፋትንም፤* ይህ አባባል በኢዮ15፥35 ላይ ካለው ጋር እንዳለ ቃል በቃል ተጽፎ ይገኛል፤ ከኢሳ33፥11፤ መዝ7፥14 ጋር ያነጻጽሩ።

59፥5 *የሸረሪት ድር፤* ቍ6 እና ኢዮ8፥14-15 ላይ የሸረሪት ድር በቀላሉ የሚበጠስ መሆኑ በአጽንዖት ተመልክቶአል።

59፥6 *በዐመፅ ሥራ፤* ቍ3፤ ኤር6፥7 ፤ሕዝ7፥11 ይመ።

59፥7-8 ኀጢአት ዐለሙን ሁሉ ያጥለቀለቀ መሆኑን ለማሳየት፣ ሐዋርያው ጳውሎስ ይህን ሐሳብ በሮሜ 3፥15-17 ላይ በከፊል ገልጾታል።

59፥7 *እግሮቻቸው ... ንጹሕ ደም ለማፍሰስ ይፈጥናሉ፤* ይህ ዐረፍተ ነገር በምሳ1፥16 ላይ እንዳለ ተጠቅሶአል። *ክፉ ሐሳብ፤* የእግዚአብሔር ሐሳብ ከዚህ የተለየ ነው (55፥7-9 ይመ)። *ማጥፋትና ማፈራረስም፤* ከ60፥18 ጋር ያስተያዩ።

59፥8 *የሰላምን መንገድ፤* ከ26፥3፡12፤ 57፥20-21፤ ሉቃ1፥79 ጋር ያነጻጽሩ። *መንገዳቸውን ጠማማ፤* የማያስተማምን ማለት ነው (መሳ5፥6 እና ማብ ይመ)።

59፥9 *ፍትሕ ... ጽድቅም፤* እዚህና በቍ14 ላይ ፍትሕና ጽድቅ በሰውኛ ዘይቤ ተገልጠዋል። ቍ4 እና ማብ፤ 1፥21 ይመ። *ጨለማ ... በድንግዝግዝታ፤* አሦር እስራኤልን በወረረች ጊዜ ሁኔታውን ለማሳየት ተመሳሳይ ቃላት ጥቅም ላይ ውለዋል (5፥30፤ 8፥21-22፤ 9፥1-2 ይመ)፤ ከ58፥8 ጋር ያስተያዩ። *ከእኛ ... እኛ፤* ነቢዩ ራሱን ከሕዝቡ ጋር ጨምሮ ይቈጥረዋል።

59፥10 *እንደ ዕውር ተደናበርን፤ ... በእኩለ ቀን፤* በዘዳ 28፥29 ላይ የተጠቀሰው አለመታዘዝ ያስከተለው ርግማን ፍጻሜ። ከኢዮ 5፥14 ጋር ያነጻጽሩ። *በብርቱዎች፤* ምናልባት ጠላቶችን ወይም ጨቋኞችን የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም።

59፥11 *እንደ ድቦች እንጮኻለን፤* ተስፋ ከመቍረጥና ከመሸነፍ የተነሣ።

59፥12 *በደላችን በፊትህ በዝቶአል፤* 58፥1 ይመ። *ዐመፀኝነታችንንም እናውቃለን፤* ልክ እንደ ዕዝራ (ዕዝ9፥6-7)፣ ኢሳይያስም የሕዝቡን ኀጢአት ይናዘዛል። ነቢዩ በዚህ ቍጥር ውስጥ ክፉ ሐሳብንና ድርጊትን ለመግለጽ በዕብራይስጥ ቋንቋ የታወቁትን ሦስት ቃሎች ተጠቅሞባቸዋል።

59፥13 *ዐምፀናል፤ ሐሰት ተናግረናል፤* 46፥8 እና ማብ ይመ። *ዘወር ብለናል፤* 1፥4 ይመ። *ግፍን፤* 30፥12 ይመ። *ውሸት፤* ቍ3-4 ይመ።

59፥14 *ፍትሕ ... እውነት፤* ይህን በምሳ8፥1-9፥12 ባለው ጥበብ በሰውኛ ዘይቤ እንዴት እንደ ተገለጠች ከሚታየው ጋር ያነጻጽሩ። *ጽድቅም በሩቁ ቆሞአል፤* ከቍ9 ጋር ያነጻጽሩ። ከ46፥13 እና ማብ ጋር ያስተያዩ።

59፥15 *እውነት፤* እንደ ገና የተሠራችው ኢየሩሳሌም በዘካ8፥3 ላይ፣ "የእውነት ከተማ" ተብላ ተጠርታለች (1፥21 እና ማብ ይመ)።

59፥16 *ማንም እንደ ሌለ፤* ለርዳታ ማለት ነው (63፥5 ይመ ከጠቅላላው የጥቅሱ ሐሳብ ጋር ተጓዳኝ ነው)፤ ከሕዝ22፥30 ጋር ያነጻጽሩ። *ተገረመ፤* በ52፥14 ላይ የተጠቀሰው አገላጋይ ካደረገው ጋር ይህን ያነጻጽሩ። *የሚማልድ፤* ይህን በ53፥12 ከተጠቀሰው አገላጋይ

ስለዚህ የገዛ ክንዱ ድነት አመጣለት፤
የራሱም ጽድቅ ደግፎ ያዘው።
[17]ጽድቅን እንደ ጥሩር አጠለቀ፤
የድነትን ቍር በራሱ ላይ ደፋ፤
የበቀልንም ልብስ ለበሰ፤
መጐናጸፊያ እንደሚደረብም ቅናትን ደረበ።
[18]እንደ ሥራቸው መጠን፣
ቍጣን ለባላጋራዎቹ፣
ፍዳን ለጠላቶቹ፣
እንደዚሁ ይከፍላቸዋል፤
ለደሴቶችም የእጃቸውን ይሰጣቸዋል።
[19]በምዕራብ ያሉት የእግዚአብሔርን ስም
ይፈራሉ፤
በፀሐይ መውጫ ያሉት ለክብሩ ይገዛሉ፤
የእግዚአብሔር እስትንፋስ እንደ ተቋተ፣
እንደ ተከማቸም ጐርፍ ይመጣልና።[ቸ]

[20]"አዳኝ ወደ ጽዮን፣
ኀጢአታቸውንም ወደ ተናዘዙት ወደ
ያዕቆብ ቤት ይመጣል"
ይላል እግዚአብሔር።

[21]"በእኔ በኩል፣ ከእነርሱ ጋር ያለኝ ቃል ኪዳን ይህ ነው" ይላል እግዚአብሔር፤ "በአንተም ላይ ያለው መንፈሴ፣ በአፍህ ያስቀመጥሁት ቃሌ ከአፍህ፣ ከልጆችህ አፍ፣ ከዘር ዘሮቻቸውም አፍ ከዛሬ ጀምሮ እስከ ዘላለም አይለይም" ይላል እግዚአብሔር።

## የጽዮን ክብር

**60** "ብርሃንሽ መጥቶአልና ተነሺ አብሪ፤
የእግዚአብሔርም ክብር ወጥቶልሻል።
[2]እነሆ፤ ጨለማ ምድርን፣
ድቅድቅ ጨለማም ሕዝቦችን ይሸፍናል፤
ነገር ግን እግዚአብሔር ወጥቶልሻል፤
ክብሩንም ይገልጥልሻል።
[3]ሕዝቦች ወደ ብርሃንሽ፣
ነገሥታትም ወደ ንጋትሽ ጸዳል ይመጣሉ።

[4]"ቀና በዪ፤ ዙሪያሽን ተመልከቺ፤
ሁሉም ተሰብስበው ወደ አንቺ ይመጣሉ፤
ወንዶች ልጆችሽ ከሩቅ፣
ሴቶች ልጆችሽም በዕቅፍ ወደ አንቺ ይመጣሉ።
[5]ከዚያም ታያለሽ፤ ታብረቀርቂያለሽ፤
ልብሽ ይዘላል፤ በደስታም ይሞላል።
በባሕሮች ያለው ሀብት ወደ አንቺ ይመጣል፤
የነገሥታትም ብልጥግና የአንቺ ይሆናል።
[6]የግመል መንጋ፣
የምድያምና የጌፌር ግልገል ግመሎች
ምድርሽን ይሞላሉ፤
ወርቅና ዕጣን ይዘው፣
የእግዚአብሔርን ምስጋና እያወጁ፣

59፥17 ኢዮ27፥6፤ ኢሳ1፥24፤9፥7፤ 63፥3፤ሕዝ5፥13፤ ኤፌ6፥14፡17፤ 1ተሰ5፥8
59፥18 ዘሌ26፥28፤ ዘኍ10፥35፤ኢሳ11፥11፤ 34፥8፤41፥5፤ ማቴ16፥27
59፥19 መዝ97፥6፤ 113፥3፤ኢሳ11፥4፤ 24፥15፤35፥2፤40፥5፤ 49፥12፤52፥10፤ 66፥18፤ማቴ8፥11
59፥20 ኢዮ19፥25፤ 22፥23፤ኢሳ1፥27፤ 52፥8፤60፥16፤63፥16፤ ኤር35፥15፤ኢል3፥21፤ ሮሜ11፥26-27፤ ሐሥ2፥38-39
59፥21 ዘፍ9፥16፤ ዘፀ4፥15፤ዘዳ29፥14፤ ኢሱ1፥8፤ኢሳ11፥2፤ 42፥6፤44፥3
60፥1 ዘፀ16፥7፤ መዝ36፥9፤118፥27፤ ኢሳ4፥5፤9፥2፤52፥2፤ ዮሐ8፥12፤ኤፌ5፥14፤ ራእ21፥11
60፥2 1ሳሙ2፥9፤ መዝ82፥5፤107፥14፤ ኢሳ8፥20፤ኤር13፥16፤ ቈላ1፥13
60፥3 ኢሳ9፥2፤ 42፥6፤44፥5፤45፥14፤ 49፥23፤ማቴ2፥1-11፤ ራእ21፥24
60፥4 ኢሳ2፥3፤ 11፥12፤43፥6፤ 49፥20-22፤ኤር30፥10
60፥5 ዘፀ34፥29፤ዘዳ33፥19፤ መሳ3፥15፤ኢሳ35፥2፤65፥13፤66፥14፤ ዘካ10፥7፤ራእ21፥26
60፥6 ዘፍ10፥7፡28፤25፥2፡4፤መሳ6፥5፤1ነገ5፥7፤ኢሳ42፥10፤ 43፥23፤ኤር6፥20፤ማቴ2፥11

[ቸ]19 ወይም፣ ጠላት እንደ ጐርፍ በሚመጣበት ጊዜ/ የእግዚአብሔር መንፈስ በውጊያ ያዋርደዋል

ምልጃ ጋር ያነጻጽሩ (የዚያኑ ማብ ይመ)። የገዛ ክንዱ ድነት አመጣለት፤ 51፥9፤52፥10 ይመ። የድነትን ትርጕም 43፥3፤ 49፥8፤ 52፥7 እና ማብ ይመ። ጽድቅ፤ በድነትና በጽድቅ መካከል ስላለው ግንኙነት 45፥8፤ 46፥13 እና ማብ ይመ።

59፥17 ጽድቅን እንደ ጥሩር፤ በኤፌ6፥14 ላይ የእግዚአብሔር የጦር መሣሪያ እንድ እማኝ ከሰይጣን ጋር ከሚዋጋበት የጦር መሣሪያ ጋር ተነጻጽሮአል። የበቀልንም ልብስ፤ ይህን በ63፥1-3 ላይ ከተገለጸው ደም ከተረጨበት ልብስ ጋር ያነጻጽሩ። የእግዚአብሔር በቀል በ34፥8 (የዚያኑ ማብ ይመ)፣ በ63፥4 ላይ ተገልጾአል፤ የእግዚአብሔር ቀን አንድ ክፍል ነው (34፥2 እና ማብ ይመ)። ቅናት፤ የእግዚአብሔርን የፍቅር ቅናት የሚያመለክት ነው (9፥7 እና ማብ 37፥32፤ 42፥13 ይመ)።

59፥18 ለባላጋራዎቹ ... ለጠላቶቹ፤ እግዚአብሔር በአሕዛብ ላይ ይፈርዳል፤ ከፋዎች እስራኤላውያንንም ይቀጣቸዋል፤ አይምራቸውም (65፥6-7፤ 66፥6፤ ኤር25፥29 ይመ)። ትሩፋኑ ብቻ ይባረካሉ (ቍ20፤ 1፥9 እና ማብ ይመ)። ለደሴቶችም፤ የ11፥11 ማብ ይመ።

59፥19 በምዕራብ ... በፀሐይ መውጫ፤ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ሲል የሚያደርገውን የማዳን ሥራ ያያሉ (40፥5፤ 45፥6፤ 52፥10 እና ማብ ይመ)። ስም፤ 30፥27 እና ማብ ይመ። እንደ ተከማቸ ጐርፍ፤ የእግዚአብሔርን መምጣት ሊያግድ የሚችል ኀይል የለም፤ አመጣጡም ጠላትን ጠራርጎ እንደሚሄድ የውሃ ሙላት ነው (30፥28 ይመ)።

59፥20 አዳኝ፤ 41፥14 እና ማብ ይመ። ወደ ጽዮን ... ይመጣል፤ ትንቢቱ ከምርኮ መመለስን ያመለክታል፤ ፍጻሜው ግን የክርስቶስን ሰው ሆኖ ወደዚህ ዓለም መምጣት ያሳያል፤ 35፥4፤ 40፥9፤ 52፥7 እና ማብ ይመ፤ ከዘካ8፥3 ጋር ያነጻጽሩ። ኀጢአታቸውንም ወደ ተናዘዙት፤ 1፥27-28 እና ማብ፤ 30፥15፤ 31፥6፤ ሕዝ18፥30-32 ይመ።

59፥21 ቃል ኪዳን፤ አገላለጹ፣ "ከአዲስ ኪዳን" ጋር ይገጥማል (42፥6 እና ማብ ኤር31፥31-34 ይመ)። መንፈሴ፤ 11፥2 እና ማብ፤ 32፥15፤ ሕዝ36፥27፤ ዮሐ16፥13 ይመ። በአፍህ ያስቀመጥሁት ቃሌ፤ ይህ ከሆነ፣ እስራኤል በእውነት የእግዚአብሔር ሕዝብ ይሆናል (51፥16 እና ኤር31፥33 ይመ)። ከአፍህ ... አይለይም፤ ኢሱ1፥8 ይመ።

60፥1-2 ክብር፤ ምናልባት ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ የደመናውን ዐምድ ለማመልከት የገባ ይሆናል፤ ይሁን እንጂ የእግዚአብሔርን የማዳን ክብር አዲስ መገለጥ ለማሳየት የገባ ነው (58፥8እና ማብ ይመ)፤ 35፥2 እና ማብ ይመ።

60፥1 ብርሃንሽ፤ 58፥8 እና ማብ ይመ። በዚህ ስፍራ እግዚአብሔር ራሱ ብርሃን እንደ ሆነ ተገልጾአል (ቍ19-20 ይመ)።

60፥2 ጨለማ፤ የሐዘን፣ የጭቈናና የኀጢአት ምልክት ነው (8፥22፤ 9፥2፤ 59፥9 ይመ)።

60፥3 ሕዝቦች ... ይመጣሉ፤ ቍ5፡10-12 እና ማብ ይመ። ይህ ጭብጥ ለመጀመሪያ ጊዜ የተገለጸው በ2፥2-4 ላይ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)። ብርሃንሽ፤ 42፥6፤ 49፥6 እና ማብ ይመ።

60፥4፤ የመጀመሪያዎቹ ሁለት ስንኞች ከ49፥18 መጀመሪያ ጋር ተመሳሳይ ሲሆኑ፣ የመጨረሻዎቹ ሁለት ስንኞች ደግሞ ከ49፥22 መጨረሻ ጋር አንድ ናቸው (የዚያኑ ማብ ይመ)። በዚያ ስፍራ የሚያመለክተው ከምርኮ መመለስን ሲሆን እዚህ ላይ ግን ሰፋ ያለ ሐሳብ ተገልጾ ይገኛል። ከሩቅ፤ ቍ9፡49፥12 እና ማብ ይመ።

60፥5 በባሕሮች ያለው ሀብት፤ ኢየሩሳሌም በሕዝቦች ሀብት ትበለጽጋለች (ቍ11፤ 61፥6፤ 66፥12፤ 18፥7፤ 23፥18፤ 45፥14 እና ማብ ይመ)። ንጉሥ ዳርዮስ ለዘሩባቤል ቤተ መቅደስ ያደረገው ርዳታ ከፊል ፍጻሜ ሊሆን ይችላል (ዕዝ6፥8-9)። አንዳንዶች ይህን ጥቅስ ወደፊት ከሚመጣው ከመሲሑ መንግሥት ሁኔታ ጋር ሲያገናኙት፣ ሌሎች ደግሞ ስፍር ቍጥር የሌላቸው አሕዛብ እንደ ውሃ ሙላት እየጐረፉ ወደ ቤተ ክርስቲያን ከሚገቡበት ሁኔታ ጋር ያያይዙታል (የ2፥2-4 ማብ ይመ)። ስለ አዲሲቱ ኢየሩሳሌም ራእ21፥26፤ ሐጌ2፥7፤ ዘካ14፥14 እና ማብ ይመ።

60፥6 የግመል መንጋ... ምድርሽን ይሞላሉ፤ ሸቀጣ ሸቀጥን ይዘው የሚጓዙትን ግመሎችን ቅፍለት ለማመልከት ሲሆን፣ ምናልባትም አንድ ጊዜ ምድያማውያን እስራኤልን ለማጥፋት ያደረጉትን ሙከራ በሽሙጥ መልክ ለማመልከት ነው (9፥4፤ መሳ6፥1-6 ይመ)። ምድያም፤ አብርሃም ኬጡራ ከተባለች ሚስቱ የወለደው ልጅ ስም ነው (ዘፍ25፥2)። ምድያማውያን ከዮርዳኖስ ማዶ ባለው ምድረ በዳ ይኖሩ ነበር። ጌፌር፤ የምድያም ልጅ ነው (ዘፍ25፥4)። ወርቅና ዕጣን፤ የሳባ ንግሥት ለንጉሥ ሰሎሞን ወርቅና ዕጣን ይዛ ሄዳለች (1ነገ10፥2)። በኤር6፥20 ላይ የሳባ ዕጣን ተጠቅሶአል፤ ከመዝ72፥10፤ ማቴ2፥11 ጋር ያነጻጽሩ። ምስጋና እያወጁ፤ በ1ነገ10፥9 ንግሥቲቱ ከተናገረችው ቃል ጋር ይህን ያነጻጽሩ።

ሁሉም ከሳባ ይመጣሉ::
[7]የቄዳር የበግ መንጋ ሁሉ ወደ አንቺ
ይሰበሰባል፤
የነባዮት አውራ በጎች ያገለግሉሻል::
እነዚህም በመሠዊያዬ ላይ ተቀባይነት የሚኖ
ራቸው መሥዋዕቶች ይሆናሉ፤
እኔም የክብር መቅደሴን ግርማ አጐና
ጽፈዋለሁ::

[8]"ርግቦች ወደ ጐጆአቸው እንደሚበሩ፣
እንደ ደመና የሚጓዙ እነዚህ እነማን ናቸው?
[9]በእርግጥ ደሴቶች እኔን ተስፋ ያደርጋሉ፤
እርሱ ክብሩን ስላጐናጸፈሽ፣
ለእስራኤል ቅዱስ፣
ለእግዚአብሔር አምላክሽ ክብር፣
ከሩቅ ወንዶች ልጆችሽን፣
ከነብራቸውና ከነወርቃቸው ለማምጣት፣
የተርሴስ መርከቦች* ቀድመው ይወጣሉ::

[10]"ባዕዳን ቅጥሮችሽን ይሠራሉ፤
ነገሥታቶቻቸው ያገለግሉሻል፤
በቍጣዬ ብመታሽም፣
ርኅራኄዬን በፍቅር አሳይሻለሁ::
[11]በሮችሽ ምንጊዜም የተከፈቱ ይሆናሉ፤
ቀንም ሆነ ሌሊት ከቶ አይዘጉም፤
ይህም ሰዎች የመንግሥታትን ብልጥግና ወደ
አንቺ እንዲያመጡ፤
ነገሥታታቸውም በድል ወደ አንቺ እንዲ
ገቡ ነው::
[12]ለአንቺ የማይገዛ ሕዝብና መንግሥት ይጠፋል፤
ፈጽሞም ይደመሰሳል::

[13]የመቅደሴን ቦታ ለማስጌጥ፣
የሊባኖስ ክብር፣
ጥዱ፣ አስታውና ባርሰነቱ በአንድነት ወደ አንቺ
ይመጣሉ፤
እግሬ የሚያርፍበትንም ስፍራ አከብራለሁ::
[14]የአስጨናቂዎችሽ ወንዶች ልጆች እየሰገዱ
ወደ አንቺ ይመጣሉ፤
የናቁሽም ሁሉ እግርሽ ላይ ይደፋሉ፣
የእግዚአብሔር ከተማ፣
የእስራኤል ቅዱስ ገንዘብ የሆንሽው ጽዮን
ብለው ይጠሩሻል::

[15]"የተተውሽና የተጠላሽ፣
ማንም ሰው የማያልፍብሽ ብትሆኚም እንኳ፣
እኔ የዘላለም ትምክሕት፣
የትውልድም ሁሉ ደስታ አደርግሻለሁ::
[16]የመንግሥታትን ወተት ትጠጫለሽ፤
የነገሥታትንም ጡት ትጠቢያለሽ፤
ከዚያም እኔ እግዚአብሔር አዳኝሽ፣
ቤዛሽም እኔ የያዕቆብ ኀያል እንደ ሆንሁ
ታውቂያለሽ::
[17]በናስ ፈንታ ወርቅ፣
በብረትም ፈንታ ብር አመጣልሻለሁ::
ስላምን ገዥሽ፣
ጽድቅንም አለቃሽ አደርጋለሁ::
[18]ከእንግዲህ በምድርሽ ሁከት፣
በጠረፎችሽም ጥፋትና መፈራረስ
አይሰማም፤
ነገር ግን ቅጥሮችሽን ድነት፣
በሮችሽንም ምስጋና ብለሽ ትጠሪያቸዋለሽ::
[19]ከእንግዲህ በቀን የፀሓይ ብርሃን
አያስፈልግሽም፤
በሌሊትም የጨረቃ ብርሃን አያበራልሽም፤
እግዚአብሔር የዘላለም ብርሃን፣

60፥7 ቍ13፤ ዘፍ25፥13፤ኢሳ18፥7፤ 19፥21፤ሕዝ20፥40፤ 43፥27፤ሶፎ3፥10፤ ሐጌ2፥3:7:9
60፥8 ኢሳ19፥1፤ 49፥21
60፥9 ቍ14፤ ዘፍ10፥4፤1ነገ10፥22፤ መዝ22፥23፤ኢሳ1፥4፤ 2፥16፤11፥11፤14፥2፤ 43፥6፤44፥23፤54፥5፤ 55፥5፤ኤር30፥19
60፥10 ዘፀ1፥11፤ ዕዝ1፥2፤መዝ102፥13፤ ኢሳ14፥1-2፤49፥8፤ 56፥6፤ራእ21፥24
60፥11 ቍ5:18፤ መዝ24፥7፤149፥8፤ ኢሳ2፥12፤61፥6፤ 62፥10፤ሚክ2፥13፤ ራእ21፥25:26
60፥12 ዘፍ27፥29፤ መዝ110፥5፤ ኢሳ11፥14፤14፥2፤ ዳን2፥34
60፥13 ቍ7፤ 1ዜና28፥2፤ዕዝ3፥7፤ ኢሳ41፥19
60፥14 ቍ9፤ ዘፍ27፥29፤32፥28፤ ኢሳ1፥26፤2፥3፤14፥2፤ ዕብ12፥22፤ራእ3፥9
60፥15 መዝ126፥5፤ ኢሳ1፥7-9፤4፥2፤ 6፥12፤33፥8፤54፥6፤ 65፥18
60፥16 ዘፍ49፥24፤ ዘፀ6፥2:7፤14፥30፤ ኢዮ19፥25፤ መዝ132፥2፤ ኢሳ25፥9፤49፥23፤ 59፥20፤66፥11:12
60፥17 1ነገ10፥21፤ መዝ85፥8፤ኢሳ9፥7፤ 66፥12፤ሐጌ2፥9
60፥18 ዘሌ26፥6፤ 2ሳሙ7፥10፤ኢሳ9፥4፤33፥6፤49፥19፤51፥19፤61፥11፤62፥7፤ኤር33፥9፤ ሶፎ3፥20 60፥19 መዝ36፥9፤85፥9፤118፥27፤ኢሳ24፥16:23፤ራ እ21፥23፤22፥5

*9 ወይም፣ የንግድ መርከቦች

ሳባ፤ በደቡብ ዐረብ የሚገኝ የባለጠጋ ምድር ነው፤ ምናልባትም የዛሬዋ የመን ወይም በዚያው አቅራቢያ ያለ ሌላ ስፍራ ሳይሆን አይቀርም (ዘፍ25፥3፤ 1ነገ10፥1-2 ይመ)::

60፥7 የቄዳር የበግ መንጋ፤ የ21፥16 ማብ ይመ:: ነባዮት፤ በኵሩ የእስማኤል ልጅ ነው (ዘፍ25፥13):: ስሙ ምናልባት በኋለኛው ዘመን በተነሣው በናባቲያን መንግሥት የተጠቀሰ ሳይሆን አይቀርም:: ያገለግሉሻል፤ ቍ10፤ 56፥6 ይመ:: ተቀባይነት የሚኖራቸው መሥዋዕቶች፤ 56፥7፤ 58፥5 እና ማብ ይመ::

60፥9 ደሴቶች እኔን ተስፋ ያደርጋሉ፤ 11፥11 እና ማብ ይመ:: ክብሩን ስላጐናጸፈሽ፤ 55፥5 እና ማብ ይመ:: ለእስራ ኤል ቅዱስ፤ ቍ14፤ 1፥4 እና ማብ ይመ:: ልጆችሽን ... ለ ማምጣት፤ 49፥22 እና ማብ ይመ:: የተርሴስ መርከቦች፤ የ2፥16 ማብ ይመ:: ከነብራቸውና ከነወርቃቸው፤ የተርሴስ መርከቦች እነዚ ህን በዓመት ሦስት ጊዜ እየጫኑ ወደ ሰሎሞን ያመጡ ነበር (1ነገ10፥22)::

60፥10 ባዕዳን ... ነገሥታቶቻቸው፤ ቍ12:14፤ 49፥7:23፤ 61፥5 ይመ:: ቅጥሮችሽን ይሠራሉ፤ 445 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነህምያ የኢየሩሳሌምን ቅጥር እንዲሠራ ንጉሥ አርጤክስስ መፍቀዱን በዐዋጅ አስነገረ (ነህ2፥8):: አንዳንዶች ይህን ሐሳብ በአሕዛብ አማኞች ከምትሠራው ቤተ ክርስቲያን ጋር ያያይዙታል (ሐሥ15፥14-16):: በቍጣዬ ... ርኅራኄዬን፤ 54፥7-8 እና ማብ ይመ::

60፥11 በሮችሽ ምንጊዜም የተከፈቱ፤ እንደ አዲሲቱ (ሰማያዊቷ) ኢየሩሳሌም ዐይነት ማለት ነው (ራእ21፥25):: ብልጥግና፤ ቍ5 ይመ::

60፥12 ሕዝብ ... ይደመሰሳል፤ ወደፊት እስራኤል ስለሚኖራት የፖለቲካ የበላይነት በ11፥14፤ 14፥2፤ 49፥23 ተጠቅሶአል (ቍ10:14 ጋር ያነጻጽሩ)::

60፥13 የመቅደሴን ቦታ ለማስጌጥ፤ ቍ7 ይመ:: የሊባኖስ ክብር፤ የሰሎሞን ቤተ መቅደስ የተሠራባቸው ትልልቅ የዝግባና የጥድ ዛፎች ከዚያ በመገኘታቸው የተሰጠ ስያሜ ነው (1ነገ5፥10:18 እንዲሁም 35፥2 ይመ)፤ ስሙ የገነነው የሰሎሞን ዘመን ክብር እንደ ገና ይመለሳል:: ጥዱ፣ አስታውና ባርሰነቱ፤ 41፥19 እና ማብ ይመ:: ዛፎቹ የተፈለጉት ምናልባትም ለሕንፃው ሥራ ሳይሆን፣ ዐልፎ ዐልፎ ለጌጥ ብቻ ሳይሆን አልቀረም:: እግሬ የሚያርፍበትን ስፍራ፤ ቤተ መቅደሱን በተለይም የቃል ኪዳኑ ታቦት፣ "የእግዚአብሔር የእግሩ መረገጫ" ነው::

60፥14 የአስጨናቂዎችሽ ... እየሰገዱ፤ 49፥7:23 እና ማብ ይመ፤ ከቍ10:12 ጋር ያነጻጽሩ:: የእግዚአብሔር ከተማ፤ ወደፊት ኢየሩሳሌም በ1፥26፤ 62፥4፤ ሕዝ48፥35፤ ዘካ8፥3፤ ዕብ12፥22 ከምትጠራበት ስም ጋር ይህን ያነጻጽሩ::

60፥15 የተተውሽና የተጠላሽ፤ 6፥11-12፤62፥4 ኤር30፥17 ይመ:: ትምክህት... ደስታ፤ 4፥2 እና ማብ ይመ::

60፥16 የነገሥታትንም ጡት ትጠቢያለሽ፤ ኢየሩሳሌም ትከብራለች፤ ምርጥ ምርጥ የሆነውን ሀብት፣ "ከነገሥታቱ ብልጥግና" ትቀበላለች (ቍ5):: ከዚያም ... የያዕቆብ፤ ይህን ዐረፍተ ነገር በሚመለከት 49፥26 እና ማብ ይመ::

60፥17 ወርቅ ... ብር፤ ወርቅና ብር በሰሎሞን ዘመን ተትረፍርፎ እንደ ነበር ሁሉ፣ በዚያን ጊዜም ይትረፈረፋል ማለት ነው (1ነገ10፥21:27):: ስለዚህ አዲሲቱ ኢየሩሳሌም እጅግ ከፍ ያለ ዋጋና ጥንካሬ ያላቸው ብረቶች ይኖሯታል፤ ከ9፥10 ጋር ያነጻጽሩ:: ሰላምን... ጽድቅንም፤ ሁለቱም መሲሑ በሚገዛበት ዘመን (9፥7) በምድሪቱ ላይ ይሰፍናሉ፤ የ48፥18 ማብ ይመ::

60፥18 ከእንግዲህ ... ሁከት፤ ከ54፥14 ጋር ያነጻጽሩ:: ጥፋትና መፈራረስ፤ 51፥19 እና ማብ ይመ:: በሮችሽንም ምስጋና፤ 26፥1 ይመ::

60፥19 የፀሓይ ... የጨረቃ፤ በራእ21፥23፤ 22፥5 ላይ እንደ ተገለጸው፣ በዚያን ጊዜ እግዚአብሔርና በጉ፣ "ዘላለማዊ ብርሃንዋ" ስለሚሆኑ አዲሲቱ ኢየሩሳሌም የፀሓይና የጨረቃ ብርሃን አያስፈ

አምላክሽም ክብርሽ ይሆናልና።
[20]ፀሓይሽ ከእንግዲህ አትጠልቅም፤
ጨረቃሽም ብርሃን መስጠቷን አታቋርጥም?
እግዚአብሔር የዘላለም ብርሃንሽ ይሆናል፤
የሐዘንሽም ቀን ያከትማል።
[21]ሕዝብሽም ሁሉ ጻድቃን ይሆናሉ፤
ምድሪቱንም ለዘላለም ይወርሳሉ፤
ለክብሬ መግለጫ ይሆኑ ዘንድ፣
የእጆቼ ሥራ፣
እኔ የተከልኋቸው ቍጥቋጦች ናቸው።
[22]ከአንቺ ታናሽ የሆነው ሺህ፣
ከሁሉም የመጨረሻው ታናሽ ኀያል መንግሥት ይሆናል፤
እኔ እግዚአብሔር ነኝ፤
ጊዜውም ሲደርስ ይህን በፍጥነት አደርጋለሁ።"

## የተወደደው የእግዚአብሔር ዓመት

**61** የጌታ የእግዚአብሔር መንፈስ በእኔ ላይ ነው፤
ለድኾች የምሥራች እንድሰብክ፣
እግዚአብሔር ቀብቶኛል።
ልባቸው የተሰበረውን እንድጠግን፣
ለምርኮኞች ነጻነትን፣
ለእስረኞች መፈታትን እንዳውጅ[*] ልኮኛል፤
[2]የተወደደውን የእግዚአብሔርን ዓመት፣
የአምላካችንንም የበቀል ቀን እንዳውጅ፣
የሚያለቅሱትን ሁሉ እንዳጽናና ልኮኛል፤
[3]በጽዮን ያዘኑትን እንዳረጋጋ፣
በዐመድ ፈንታ፣
የውበት አክሊል እንድደፋላቸው፣
በልቅሶ ፈንታ፣
የደስታ ዘይት በራሳቸው ላይ እንዳፈስላቸው፣
በትካዜ መንፈስ ፈንታ፣
የምስጋና መጐናጸፊያ እንድደርብላቸው ልኮኛል፤
እነርሱም የክብሩ መግለጫ እንዲሆኑ፣
እግዚአብሔር የተከላቸው፣
የጽድቅ ዛፎች ተብለው ይጠራሉ።
[4]የጥንት ፍርስራሾችን መልሰው ይሠራሉ፤
በቀድሞ ጊዜ የወደሙትን መልሰው ያቆማሉ፤
ከብዙ ትውልድ በፊት የወደሙትን
ፍርስራሽ ከተሞች እንደ ገና ይሠራሉ።
[5]መጻተኞች የበግ መንጎቻችሁን ያግዳሉ፤
ባዕዳን በዕርሻችሁና በወይን ተክል
ቦታችሁ ላይ ይሠሩላችኋል።
[6]እናንተም የእግዚአብሔር ካህናት ተብላችሁ
ትጠራላችሁ፤
የአምላካችን ባሮች ትባላላችሁ፤
የመንግሥታትን ሀብት ትመገባላችሁ፤
በብልጽግናቸውም ትኰራላችሁ።
[7]ሕዝቤ በኀፍረታቸው ፈንታ፣
ዕጥፍ ይቀበላሉ፤
በውርደታቸው ፈንታ፣
በርስታቸው ደስ ይላቸዋል፤
የምድራቸውንም ዕጥፍ ርስት ይወርሳሉ፤
ዘላለማዊ ደስታም የእነርሱ ይሆናል።
[8]"እኔ እግዚአብሔር ፍትሕን ስለምወድ፣
ዝርፊያንና በደልን እጠላለሁ፤
በታማኝነቴም የሚገባቸውን እሰጣቸዋለሁ፤
ከእነርሱም ጋር የዘላለም ኪዳን አደርጋለሁ።

60፥20 ኢሳ30፥19፡26፤35፥10፤ራእ7፥17 60፥21 ዘፀ15፥17፤ ዘሌ10፥3፤ኢዮ10፥3፤ መዝ8፥6፤37፥11፡22፤ 44፥2፤80፥8-11፤ ኢሳ4፥3፤19፥25፤ 26፥2፤44፥23፤ 49፥8፤ 57፥13፤61፥7፤ 65፥9፤ኤር32፥41፤ አሞ9፥15፤ዘካ8፥12፤ ማቴ15፥13፤ ኤፌ2፥10፤ራእ21፥27 60፥22 ዘፍ12፥2፤ ዘዳ1፥10፤ኢሳ5፥19 61፥1 ዘሌ25፥10፤ 2ሳሙ18፥26፤ 2ነገ22፥19፤ኢዮ5፥16፡18፤ መዝ45፥7፤68፥6፤ ኢሳ11፥2፤40፥9፤ 49፥9፤50፥4፤ ዳን9፥24-26፤ ማቴ11፥5፤ሉቃ7፥22፤ ሐሥ4፥26፤2ቆሮ3፥17 61፥2 ኢዮ5፥11፤ ኢሳ1፥24፤40፥1፤49፥8፤ ማቴ5፥4፤ ሉቃ4፥18-19፤6፥21 61፥3 ሩት3፥3፤ ኢዮ2፥8፤መዝ1፥3፤ 92፥12-13፤ኢሳ1፥6፤ 3፥23፤44፥23፤ ኤር31፥13፤ማቴ5፥4፤ 15፥13፤1ቆሮ3፥9፤ ዕብ1፥9 61፥4 ኢሳ44፥26፤ 51፥3፤65፥21፤ ሕዝ36፥33፤አሞ9፥14፤ ዘካ1፥16-17 61፥5 ኢሳ14፥1-2፤ 56፥6 61፥6 ዘፀ19፥6፤ ዘዳ33፥19፤ኢሳ60፥11፤ 1ጴጥ2፥5 61፥7 ዘዳ21፥17፤መዝ126፥5፤ኢሳ25፥9፤29፥22፤40፥2፤ 41፥11፤ 60፥21 61፥8 ዘፍ9፥16፤መዝ11፥7፤ኢሳ1፥17፤5፥16፤42፥6፤ ዕብ13፥20

[*]1 ዕብራይስጡ ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሰብዓ ሊቃናት ትርጉም ግን፣ *ዕውራንን ከጨለማ አመጣቸው ዘንድ* ይላል።

ልጋትም። *ክብርሽ፤* ቍ1-2 እና ማብ ይመ፤ ዘካ2፥5 ይመ።

60፥20 *ፀሓይሽ ከእንግዲህ አትጠልቅም፤* በዚያ ጨለማ አይኖርም (ከራእ 22፥5 ጋር ያነጻጽሩ)፤ የደስታና የድነት ብርሃን ብቻ እንጂ (58፥8 እና ማብ ይመ)። *የሐዘንሽም ቀን ያከትማል፤* 25፥8፤ 35፥10፤ 51፥11፤ 65፥19፤ ራእ21፥4 ይመ።

60፥21 *ሕዝብሽም ሁሉ ጻድቃን፤* በዚያ የሚኖሩት የዳኑ ብቻ ናቸውና (4፥3፤ 35፥8፤ ራእ 21፥27 ይመ)። *ምድሪቱንም ለዘላለም ይወርሳሉ፤* ፍጹም ወደ ሆነው በረከት ይገባሉ ማለት ነው (49፥8 እና ማብ 57፥13፤ 61፥7፤ መዝ37፥11፡22 ይመ። *ለክብሬ መግለጫ፤* የእግዚአብሔር የማዳን ሥራ መግለጫዎች ናቸው፤ 49፥3፤ 61፥3 የ35፥2፤ 40፥5 ማብ ይመ። *የእጆቼ ሥራ፤* ሸክላ ሠሪ ሸክላውን እንደሚያበጅ፣ እግዚአብሔር ፈጥሮአቸዋል (64፥8፤ 29፥23፤ 45፥11 ይመ)። *እኔ የተከልኋቸው ቍጥቋጦች፤* ይህን በ5፥2፡7 ላይ ከተጠቀሰው የወይን ተክል ጋር ያነጻጽሩ (11፥1 ይመ)።

60፥22 *ታናሽ የሆነው አንድ ሺህ፤* 51፥2፤54፥3 እና ማብ ይመ። በዘሌ26፥8 ላይ ያለው በረከት ከዚህ ጋር ተመሳሳይ ነው። *በፍጥነት አደርጋለሁ፤* ከ5፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

*61፥1-2፤* ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ናዝሬት በነበረው ምኵራብ ውስጥ ይህን ቃል ስለ ራሱ ጠቅሶ ተናግሮታል (ሉቃ4፥16-21 ይመ፤ ከማቴ11፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

61፥1 *የጌታ እግዚአብሔር፤* 50፥4-5፡7፡9 እና ማብ ይመ። *መንፈስ በእኔ ላይ ነው፤* ይህ ዐረፍተ ነገር በተወሰነ ደረጃ ኢሳይያስን የሚያመለክት መስሎ ቢታይም፣ አገልጋዩን መሲሕ የሚመለከት ነው (ስለ እርሱ በ42፥1 የተናገረውን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ፤ 11፥2፤ 48፥16 እና ማብ ይመ)። *ለድኾች፤* ከ11፥4፤ 29፥19 ጋር ያነጻጽሩ። *የምሥራች፤* 40፥9 እና ማብ ይመ። *ቀብቶኛል፤* 45፥1 እና ማብ ይመ። *የተሰበረውን እንድጠግን፤* 30፥26 እና ማብ ይመ። *ለምርኮኞች ነጻነትን፤* በዘሌ25፥10 ላይ በኢዮቤልዩ ዓመት ነጻነት በተግባር ይገለጣል (49፥8 እና ማብ ይመ)። ከኀጢአት ነጻ ከመውጣት በስተ ጀርባ ከባቢሎን ነጻ መውጣት አለ (42፥7 እና ማብ ይመ)።

61፥2 *የእግዚአብሔርን ዓመት፤* "የድነት ቀን" (49፥8) እና "የምቤዠበት ዓመት" (63፥4) ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ ነው፤ በሉቃ 4፥19-20 ክርስቶስ ንግግሩን ያበቃው እዚህ ቃል ላይ ሲደርስ ነው። እዚህ ላይ ያቆመው ምናልባትም ከዳግም ምጽአቱ በፊት፣ "የበቀል ዓመት" ሊኖር ስለማይችል ይሆናል (34፥2፡8 እና ማብ ይመ)። *የበቀል ቀን፤* 34፥2፡8 እና ማብ ይመ። *የሚያለቅሱትን ሁሉ እንዳጽናና፤* 49፥13፤ 57፥19 እና ማብ 66፥10፤ ኤር31፥13፤ ማቴ5፥4 ይመ።

61፥3 *የውበት አክሊል፤* የራስ ጥምጥም ወይም እንደ ሻሽ ያለ ነገር ሕዝ24፥17 ይመ። በ3፥20 ላይ እንደ ተጠቀሰው የኢየሩሳሌም ሴቶች ውብ የራስ ሻሻቸውን መጣል ነበረባቸው። *የደስታ ዘይት፤* ደስ የሚያሰኝ ሁኔታ ባጋጠመ ጊዜ ቅባት መቀባት የተለመደ ነበር (መዝ23፥5፤ 45፥7፤ 104፥15፤ 133፥1-2፤ 2ሳሙ14፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። 1፥6 እና ማብ ይመ። *የምስጋና መጐናጸፊያ፤* በ59፥17 ላይ ከተጠቀሰው "የበቀል መጐናጸፊያ" ጋር ይህን ያነጻጽሩ። *መግለጫ እንዲሆኑ ... የተከላቸው፤* 60፥21 እና ማብ ይመ። *የጽድቅ ዛፎች፤* ከ1፥30 ጋር ያነጻጽሩ።

61፥4 *የጥንት ፍርስራሾችን ... ፍርስራሽ ከተሞች፤* 58፥12 እና ማብ ይመ።

61፥5 *መጻተኞች ... ባዕዳን፤* 14፥1-2፤ 56፥3፤ 60፥10 እና ማብ ይመ።

61፥6 *የእግዚአብሔር ካህናት፤* 66፥21 ይመ። እውነተኛይቱ እስራኤል በአሕዛብ መካከል ያለች፣ "የካህናት መንግሥት" ትሆናለች (ዘጸ19፥6 እና ማብ ይመ)። *ባሮች፤* ካህናት ለማለት ነው፤ 1ነገ8፥11 ይመ። *የመንግሥታትን ሀብት፤* 60፥5 እና ማብ ይመ።

61፥7 *በኀፍረታቸው ... በውርደታቸው፤* 45፥17፤ 54፥4 ይመ። *ዕጥፍ፤* በኵር የሆነ ሁሉ ከውርሱ/ከርስቱ ዕጥፍ ድርሻ ይቀበላል (ዘዳ21፥17፤ ዘካ9፥12 ይመ)። በ40፥2 ላይ እስራኤል የምትቀበለውን ዕጥፍ ቅጣት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ።

61፥8 *ፍትሕን ስለምወድ፤* ከ30፥18፤59፥15 ጋር ያነጻጽሩ። *ዝርፊያንና በደልን፤* ገዥዎቿ በእስራኤል ላይ ክፉ ነገር ያደርሱባት ነበር። ከ42፥24፤59፥18 ጋር ያነጻጽሩ። *የዘላለም ኪዳን፤* ምናልባትም አዲሱን ኪዳን ለመጥቀስ ይሆናል (55፥3፤ 59፥21 እና ማብ ይመ።

[9]ዘሮቻቸው በመንግሥታት፣
ልጆቻቸውም በሕዝቦች ዘንድ የታወቁ
ይሆናሉ፤
የሚያዩአቸውም ሁሉ፣
*እግዚአብሔር* የባረካቸው ሕዝብ እንደ ሆኑ
ያውቃሉ።

[10]*በእግዚአብሔር* እጅግ ደስ ይለኛል፤
ነፍሴ በአምላኬ ሐሤት ታደርጋለች፤
ሙሽራ ራሱን እንደሚያሳምር፣
ሙሽራዪቱም በዕንቆቿ እንደምታጌጥ፣
የድነትን ልብስ አልብሶኛል፤
የጽድቅንም መጐናጸፊያ ደርቦልኛል።
[11]ምድር ቡቃያ እንደምታበቅል፣
የተክል ቦታ ችግኝ እንደሚያፈላ፣
ጌታ *እግዚአብሔርም* በመንግሥታት ሁሉ ፊት፣
ጽድቅንና ምስጋናን ያበቅላል።

### አዲሱ የጽዮን ስም

# 62

ጽድቋ እንደ ማለዳ ወጋገን
እስኪፈነጥቅ፣
ድነቷ እንደሚያንጸባርቅ ፋና እስኪታይ፣
ስለ ጽዮን ዝም አልልም፤
ስለ ኢየሩሳሌምም ጸጥ አልልም።
[2]መንግሥታት ጽድቅሽን፣
ነገሥታት ክብርሽን ያያሉ፤
*የእግዚአብሔር* አፍ በሚያወጣልሽ፣
በአዲስ ስም ትጠሪያለሽ።
[3]*በእግዚአብሔር* እጅ የክብር አክሊል፣
በአምላክሽም እጅ የመንግሥት ዘውድ
ትሆኛለሽ።
[4]ከእንግዲህ፣ "የተተወች" ብለው አይጠሩሽም፤
ምድርሽም፣ "የተፈታች" አትባልም፤
ነገር ግን፣ "ደስታዬ በእርሷ" ትባያለሽ፤
ምድርሽም፣ "ባለ ባል" ትባላለች፤
*እግዚአብሔር* በአንቺ ደስ ይለዋል፤
ምድርሽም ባለ ባል ትሆናለች።
[5]ጐልማሳ ድንግሊቱን እንደሚያገባ፣
ልጆችሽ[a] እንዲሁ ያገቡሻል፤
ሙሽራ በሙሽራዪቱ ደስ እንደሚለው፣
አምላክሽም በአንቺ ደስ ይለዋል።

[6]ኢየሩሳሌም ሆይ፤ ዘብ ጠባቂዎችን በቅጥሮችሽ
ላይ አቁሜአለሁ፤
ቀንም ሆነ ሌሊት ፈጽሞ አይታክቱም።
እናንት ወደ *እግዚአብሔር* አቤት፣ አቤት
የምትሉ፣
ፈጽሞ አትረፉ፤
[7]ኢየሩሳሌምን እስኪያጸናት፣
የምድርም ምስጋና እስኪያደርጋት ዕረፍት
አትስጡት።

[8]*እግዚአብሔር* በቀኝ እጁ፣
በኀያል ክንዱም እንዲህ ሲል ምሎአል፤
"ከእንግዲህ እህልሽን፣
ለጠላቶችሽ መብል እንዲሆን አልሰጥም፤
ከእንግዲህ የደከምሽበትን፣
አዲስ የወይን ጠጅ ባዕዳን አይጠጡትም።
[9]ነገር ግን መከሩን የሰበሰቡ ይበሉታል፤
*እግዚአብሔርንም* ያመሰግናሉ፤
የወይኑን ፍሬ የለቀሙም በመቅደሴ
አደባባዮች ይጠጡታል።"

[10]ዕለፉ፤ በበሮቹ በኩል ዕለፉ፤
ለሕዝቡ መንገድ አዘጋጁ፤
አስተካክሉ፤ ጐዳናውን አስተካክሉ፤
ድንጋዩን አስወግዱ፤
ለመንግሥታትም ምልክት አሳዩ።

[11]*እግዚአብሔር* እስከ ምድር ዳርቻ፣
እንዲህ ሲል ዐውጆአል፤
"ለጽዮን ሴት ልጅ፣
'እነሆ፤ አዳኝሽ መጥቶአል፤

[a]5 ወይም፣ ገንቢዎችሽ

61፥9 ዘፍ12፥2፤ ዘዳ28፥3-12፤ ኢሳ43፥5፤48፥19
61፥10 ዘዕ39፥28፤ ኢዮ27፥6፤መዝ2፥11፤ 132፥9፤ኢሳ7፥13፤ 25፥9፤49፥18፤52፥1፤ ዕን3፥18፤ሉቃ1፥47፤ ራእ19፥8፤21፥2
61፥11 ዘፍ47፥23፤ ኢሳ45፥8፤58፥11
62፥1 አስ4፥14፤ ኢዮ11፥17፤ መዝ50፥2፤67፥2፤ 83፥1፤ኢሳ1፥26፤ 45፥8
62፥2 ዘፍ32፥28፤ መዝ67፥2፤ኢሳ1፥26፤ 40፥5፤45፥14፤52፥10፤ ራእ2፥17፤3፥12
62፥3 ኢሳ28፥5፤ 1ተሰ2፥19
62፥4 ዘሌ26፥43፤ 2ነገ21፥1፤ኢሳ6፥12፤ 49፥19፤51፥19፤54፥5፡ 6፤65፥19፤ኤር3፥14፤ 32፥41፤ሆሴ2፥19፤ ሶፎ3፥17፤ሚል3፥12
62፥5 ዘዳ28፥63፤ መሐ3፥11፤ኢሳ65፥19፤ ኤር31፥12፤ሶፎ3፥17
62፥6 መዝ132፥4፤ ኢሳ52፥8፤ዕብ13፥17
62፥7 ዘዳ26፥19፤ ኢሳ60፥18፤ ማቴ15፥21-28፤ ሉቃ18፥1-8
62፥8 ዘፍ22፥16፤ ዘዳ28፥30-33፤ ኢሳ1፥7፤14፥24፤ 49፥18
62፥9 ዘሌ23፥39፤ ዘዳ12፥7፤ኢሳ1፥19፤ ኢዩ2፥26፤አሞ9፥14
62፥10 መዝ24፥7፤ ኢሳ11፥10፡16፤ 57፥14፤60፥11
62፥11 ዘዳ30፥4፤ መዝ9፥14፤ኢሳ35፥4፤

ከኤር31፥35-37፤ 32፥40 ጋር ያነጻጽሩ)።

61፥9 *እግዚአብሔር የባረካቸው ሕዝብ፤* 44፥3፤ 65፥23 ይመ፤ በዘፍ12፥1-3 ለአብርሃም የገባውን ቃል ኪዳን ይመ።

61፥10 ይህን የምትናገረው ጽዮን ራሷ ልትሆን ትችላለች። *የድነትን ልብስ፤* ቁ3፡52፥1 እና ማብ ይመ። *ራሱን እንደ ካህን፤* ሻሽ ወይም ጥምጥም በማድረግ ለማለት ነው (የቁ3 ማብ ይመ)። *ሙሽራይቱም በዕንቆቿ፤* 49፥18 እና ማብ ይመ።

61፥11 *ቡቃያ እንደምታበቅል፤* ከ55፥10 ጋር ያነጻጽሩ። *ጽድቅንና ምስጋናን ያበቅላል፤* 45፥8 እና ማብ ይመ።

*62፥1፡6፤* (እኔ) የሚለው ራሱ እግዚአብሔር ነው።

62፥1 *ዝም አልልም፤ ... ጸጥ አልልም፤* ቁ6፤ 42፥14፤ 57፥11 እና ማብ።

*64፥12፤65፥6፤* መዝ28፥1 ይመ። *ጽድቋ ... ድነቷ፤* 46፥13 እና ማብ ይመ። *ማለዳ፤* ከ58፥8 ጋር ያነጻጽሩ።

62፥2 *መንግሥታት ... ክብርሽን ... ያያሉ፤* 52፥10፤ 40፥5፤ 60፥3 እና ማብ ይመ፡ ኢየሩሳሌምን ለማለት ነው (ቁ1፡6 ይመ)። *በአዲስ ስም፤* አዲሱን ሕይወቷን የሚገልጽ ነው (ቁ4፡12፤ 1፥26፤ 60፥1፤ ዘፍ32፥28 እና ማብ ይመ)።

62፥3 *የክብር አክሊል፤* በ28፥5 ላይ እግዚአብሔር የሕዝቡ "የክብር አክሊል" መሆኑ ተገልጾአል (ከዘካ9፥16 ጋር ያነጻጽሩ)።

62፥4 *የተተወች ... የተፈታች፤* 54፥6-7፤ 60፥15 እና ማብ ይመ። *ደስ የምሰኝባት፤* ይህን ዕብራይስጥ "ሐፍሴባ" ይበላል፤ ቃሉ የይሁዳ ንጉሥ የሕዝቅያስ ሚስት ስም ነው (2ነገ21፥1)። *ባል ያገባች፤* የእግዚአብሔርና የእስራኤል ግንኙነት እንደ ገና ይጠነክራል ማለት ነው፤ 50፥1 እና ማብ ይመ።

62፥5 *ወንዶች ልጆችሽም ... ያገቡሻል፤* እስራኤላውያን ትተውት የነበረውን ምድር መልሰው እንደሚይዙት ያመለክታል፤ ከ54፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ49፥1 ማብ ይመ።

62፥6 *ዘብ ጠባቂዎችን፤* የምሥራች ቃል ይዞ የሚመጣውን መልእክተኛ የሚጠብቁትን (በተለይም ነቢያትን፤ 56፥10፤ ይመ 52፥8 እና ማብ ይመ)። *አይታክቱም፤* እግዚአብሔር ዝም እንዳይላቸው ጸሎታቸውን አያቋርጡም (ቁ1)፤ እርሱም ኢየሩሳሌምን ከመታደግ ወደ ኋላ አይልም። *ፈጽሞ አትረፉ፤* ዳዊት የታቦቱን ማደሪያ ቦታ እስኪያገኝ ድረስ ያለ ማቋረጥ ያደረገውን ከባድ ጸሎት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (መዝ132፥1-5)።

62፥7 *የምድርም ምስጋና፤* ከኤር33፥9፤ ሶፎ3፥19-20፤ ጋር ያነጻጽሩ 60፥3 እና ማብ ይመ።

62፥8 *ምሎአል፤* ከ45፥23፤54፥9 ጋር ያነጻጽሩ። *በኀያል ክንዱም፤* 51፥9 እና ማብ ይመ። *እህልሽን ለጠላቶችሽ ... አዲስ የወይን ጠጅ ባዕዳን አይጠጡትም፤* ሙሴ በዘሌ26፥16፤ ዘዳ28፥33 የተናገረው ርግማን ነው። 52፥1 እና ማብ፤ ኤር5፥17 ይመ።

62፥9 *ይበሉታል ... ይጠጡታል፤* 65፥13፡21-23 ይመ። *በመቅደሴ አደባባዮች፤* በበዓል ቀን ወይም ዐሥራታቸውን ለጌታ በሚያቀርቡት ቀን ሊሆን ይችላል (ዘሌ23፥39-40፤ ዘዳ14፥22-26)።

62፥10 *ዕለፉ ... ዕለፉ፤* የ40፥1 ማብ ይመ። *በበሮቹ፤* ምናልባትም የባቢሎን በሮች ማለት ይሆናል (ከ48፥20፤ ሚክ2፥12-13 ጋር ያነጻጽሩ)። *መንገድ አዘጋጁ... ጐዳናውን አስተካክሉ፤* 40፥3፤ 49፥11 እና ማብ ይመ። *ድንጋዩን አስወግዱ፤* 57፥14 ይመ። *ምልክት፤* 5፥26 እና ማብ ይመ።

62፥11 *እስከ ምድር ዳርቻ፤* 11፥12፤ 49፥6 እና ማብ ይመ። *ለጽዮን ሴት ልጅ፤* ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን የሚገልጽ ነው። *አዳኝሽ መጥቶአል፤* 40፥9 እና ማብ፤ ዘካ9፥9፤ ማቴ21፥5፤ 43፥3 እና

ዋጋሽ በእጁ አለ፤
ዕድል ፈንታሽም ከእርሱ ጋር ነው’ በሏት።”
[12]እነርሱም ቅዱስ ሕዝብ፣
እግዚአብሔር የተቤዣቸው ተብለው
ይጠራሉ፤
አንቺም የምትፈለግ፣
ከእንግዲህም የማትተው ከተማ ትባያለሽ።

**እግዚአብሔር የሚቤዥበትና የሚበቀልበት ቀን**

**63** ይህ ከኤዶም፣
ቀይ የተነከረ መጐናጸፊያ ለብሶ
ከባሶራ የሚመጣ ማን ነው?
ይህ ክብርን የተጐናጸፈ፣
በኀይሉ ታላቅነት እየተራመደ የሚመጣውስ
ማን ነው?

“በጽድቅ የምናገር፣
ለማዳንም ኀይል ያለኝ፣ እኔው ነኝ።”

[2]መጐናጸፊያህ፣ ለምን
በወይን መጭመቂያ ወይን እንደሚረግጡ
ሰዎች ልብስ ቀላ?

[3]“እኔ በመጭመቂያው ወይኑን ብቻዬን ረገጥሁ፤
ከመንግሥታት ማንም ከእኔ ጋር አልነበረም፤
በቍጣዬ ረገጥኋቸው፤
በመዓቴም ጨፈለቅኋቸው፤
ደማቸው በመጐናጸፊያዬ ላይ ተረጭቶአል፤
ልብሴንም በክዬዋለሁ።
[4]የበቀል ቀን በልቤ አለ፤
የምቤዥበትም ዓመት ደርሶአል።
[5]ተመለከትሁ፤ የሚረዳ ግን አልነበረም፤
የሚያግዝ ባለመኖሩም ተገረምሁ፤
ስለዚህ የገዛ ክንዴ ድነትን አመጣልኝ፤
የገዛ ቍጣዬም አጸናኝ፤
[6]መንግሥታትን በቍጣዬ ረጋገጥሁ፤
በመዓቴም አሰከርኋቸው፤
ደማቸውንም በምድር ላይ አፈሰስሁ።”

**ውዳሴና ጸሎት**

[7]የእግዚአብሔርን ቸርነት፣
እግዚአብሔር ስላደረገልን ሁሉ፣
ስለሚመሰገንበት ሥራው፣
እንደ ፍቅሩና እንደ ቸርነቱ መጠን፣
ለእስራኤል ቤት ያደረገውን፣
አዎን፣ ስላደረገው መልካም ነገር እናገራለሁ።
[8]እርሱም፣ ‘እርግጥ ነው፤ እነርሱ ሕዝቤ
ናቸው፤
የማይዋሹኝ ወንዶች ልጆቼ ናቸው” አለ።
ስለዚህም አዳኝ ሆነላቸው።
[9]በጭንቃቸው ሁሉ ተጨነቀ፤
የፊቱም መልአክ አዳናቸው፤
በፍቅሩና በምሕረቱ ዋጃቸው፤
በቀደመው ዘመን ሁሉ አነሣቸው፤ ተሸከ
ማቸውም።
[10]እነርሱ ግን ዐመፁ፤
ቅዱስ መንፈሱንም አሳዘኑ፤
ስለዚህ ተመልሶ ጠላት ሆናቸው፤
እርሱ ራሱ ተዋጋቸው።

[11]ከዚያም ሕዝቡ የጥንቱን ዘመን፣
የሙሴንና የሕዝቡን ጊዜ እንዲህ በማለት
አስታወሱ፤
የበጎቹን እረኛ፣
ከባሕሩ ያወጣቸው እርሱ የት አለ?
ቅዱስ መንፈሱንም፣
በመካከላቸው ያኖረ እርሱ የት አለ?
[12]የከበረው ኀያል ክንድ፣
በሙሴ ቀኝ እጅ ላይ እንዲያርፍ አደረገ፤
ለራሱ የዘላለም ዝና እንዲሆንለት፣
ውሆችን በፊታቸው ከፈለ።

40፥10፤ዘካ9፥9፤ ማቴ21፥5፤ራእ22፥12
62፥12 ዘፍ32፥28፤ ዘፀ19፥6፤መዝ27፥9፤ 106፥10፤ኢሳ35፥9፤ 42፥16፤44፥23፤ 54፥6፤1ጴጥ2፥9
63፥1 ቍ5፤ ዘፍ36፥33፤ 2ዜና28፥17፤ ኢዮ9፥4፤ኢሳ11፥14፤ 45፥24፤46፥13፤51፥5፤ ኤር42፥11፤አሞ1፥12፤ ሶፎ3፥17፤ራእ19፥13
63፥2 ዘፍ49፥11
63፥3 መሳ6፥11፤ ኢዮ40፥12፤ መዝ108፥13፤ኢሳ5፥5፤ 22፥5፤ራእ14፥20፤ 19፥13
63፥4 ኢሳ1፥24፤ ኤር50፥15
63፥5 2ነገ14፥26፤ መዝ44፥3፤98፥1፤ ኢሳ33፥2፤41፥28፤ 59፥16
63፥6 ኢዮ40፥12፤ መዝ108፥13፤ ኢሳ29፥9፤4፥3፤ ሰቆ4፥21
63፥7 ዘፀ18፥9፤ መዝ51፥1፤ኢሳ54፥8፤ ኤፌ2፥4
63፥8 ዘፀ14፥30፤ መዝ100፥3፤ኢሳ25፥9፤ 51፥4
63፥9 ዘፀ14፥19፤ 33፥14፤ዘዳ1፥31፤ 7፥7-8፤32፥7፤ዕዝ9፥9፤ ኢዮ37፥23፤መዝ28፥9፤ ኢሳ48፥20
63፥10 ኢሱ10፥14፤ መዝ51፥11፤78፥17፤ 106፥40፤ኢሳ10፥4፤ ሕዝ20፥8፤ ሐሥ7፥39-42፡51፤ ኤፌ4፥30
63፥11 ዘፀ14፥22፡ 30፤ዘኍ11፥17፤ መዝ77፥20
63፥12 ዘፍ49፥24፤ ዘፀ3፥20፤14፥21-22፤ መዝ102፥12፤ኢሳ11፥15፤ 55፥13፤ ኤር13፥11

ማብ ይመ። ዋጋሽ ... ዕድል ፈንታሽም፤ 40፥10 እና ማብ ይመ።

62፥12 ቅዱስ ሕዝብ፤ 4፥3፤ ዘፀ19፥6 እና ማብ ይመ። የተቤዣቸው፤ 35፥9 እና ማብ ይመ። የምትፈለግ ... የማትተው፤ ቍ4 ይመ።

63፥1 ከኤዶም፤ 21፥11፤34፥5 እና ማብ ይመ። እዚህ ላይ ኤዶም የሚለው ቃል የእግዚአብሔር ሕዝብ ጠላት የሆነውን ዓለም ይወክላል። ቀይ የተነከረ፤ በራእ 19፥13 ላይ ክርስቶስ በዳግም ምጽአቱ ጦርነት በሚያካሂድበት ጊዜ “ደም የተነከረውን ልብሱን” ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ። ከባሶራ፤ 34፥6 እና ማብ ይመ። በጽድቅ ... ለማዳንም ኀይል፤ 45፥8፤ 46፥13፤ 59፥16 እና ማብ ይመ።

63፥2 ለምን ...? እዚህ ላይ ኢሳይያስ ለጥያቄው መልስ ይሰጣል። በወይን መጭመቂያ ወይን እንደሚረግጡ፤ 16፥10 እና ማብ ይመ።

63፥3 በመጭመቂያው ... ረገጥሁ፤ በሰቆ1፥15፤ ኢዩ3፥13፤ ራእ14፥17-20፤ 19፥15 ፍርድን የሚገልጽ ዘይቤያዊ አነጋገር ነው። በቍጣዬ ... በመዓቴም፤ የጌታን ቀን ያመለክታል። ቍ6፤ 13፥3፤ 34፥2 እና ማብ ይመ።

63፥4 የበቀል ቀን ... የምቤዥበትም ዓመት፤ 61፥2 እና ማብ ይመ። እግዚአብሔር በጠላት ላይ የሚፈርድበት ቀን ሕዝቡን የሚታደግበት ዓመትም ማለት ነው፤ 35፥9፤ 41፥14 እና ማብ ይመ።

63፥5፤ ከ59፥16 ጋር ተጓዳኝ መሆኑንና ማብ ይመ። ቍጣዬም፤ ይህ በ59፥16 ላይ ጽድቅ ተብሎአል፤ የእግዚአብሔር ጽድቅና ቅድስና ከተደፈረ ፍርድ መከተሉ አይቀሬ ነው።

63፥6 አሰከርኋቸው፤ የቍጣውን ጽዋ ስለ ጠጡ ሰከሩ (51፥17 እና ማብ ይመ)። ደማቸውንም ... አፈሰስሁ፤ በዚህ ስፍራ ጦርነቱ በ34፥6 ላይ እንደ ተገለጸው ከመሥዋዕት ጋር ተነጻጽሮአል።

63፥7-64፥12፤ እግዚአብሔር በኢየሩሳሌም ቅጥሮች ላይ እንዳስቀመጣቸው ጠባቂዎች ሁሉ፣ ሕዝቡን ለመቤዠት የገባውን ቃል በጭንቀና በመከራው ጊዜ እግዚአብሔር እንዲፈጽም ኢሳይያስ ያቀረበው ጸሎት ነው (62፥6 እና ማብ ይመ)፤ ይህም ሕዝቡ በአንድነት ከሚያሰማው ሰቆቃ ጋር ተመሳሳይ ነው (ለምሳሌ መዝ44 ይመ)።

63፥7 ቸርነት፤ እግዚአብሔር ለእስራኤል የገባውን የተስፋ ቃል ሲፈጽም የማይናወጥ ፍቅሩን የሚገልጽበት አንዱ መንገድ ነው። መልካም ነገር፤ ከኢሱ21፥45፤ 1ነገ8፥66 ጋር ያነጻጽሩ። እንደ ፍቅሩና፤ 54፥7-8፡10 እና ማብ ይመ።

63፥8 ሕዝቤ ... የማይዋሹኝ ወንዶች ልጆቼ፤ ይሁን እንጂ 1፥2-4 ይመ። አዳኝ፤ 43፥3 እና ማብ ይመ።

63፥9 በጭንቃቸው ... ተጨነቀ፤ በግብፅ የነበረው ሥቃይና በመሳፍንት ዘመን የነበረው መከራ ምናልባት እዚህ ላይ ሳይታሰብ አልቀረም (መሳ10፥16 ይመ)። የፊቱም መልአክ አዳናቸው፤ ዘፀ 23፥20-23፤ 33፥14-15 ይመ። ዋጃቸው፤ 41፥14፤ 43፥1 እና ማብ ይመ። አነሣቸው፤ ተሸከማቸውም፤ ልክ እንደ አባት ማለት ነው (ዘዳ1፥31፤ 32፥10-12 ይመ)።

63፥10 ዐመፁ፤ ይህን ያደረጉት በምድረ በዳ ነው (1፥2 እና ማብ፤ 30፥1 ይመ፤ ዘኍ20፥10፤ መዝ78፥40 ይመ)። ቅዱስ መንፈሱንም አሳዘኑ፤ መዝ106፥33፤ ከኢሳ11፥1-2፤ 42፥1 ጋር ያነጻጽሩ። ጠላት ሆናቸው፤ 43፥28 እና ማብ ይመ።

63፥11 ከባሕሩ፤ ቀይ ባሕርን ነው (50፥2 እና ማብ 51፥10 ይመ)። እረኛ፤ ሙሴን ነው። ቅዱስ መንፈሱንም፤ የ51፥11 ማብ ይመ፤ መንፈስ ቅዱስ በሙሴና በሰባው የእስራኤል አለቆች ላይ ዐርፎ ነበር (ዘኍ11፥17፡25)፤ ቍ14 ይመ።

63፥12 ኀያል ክንድ፤ 51፥9 እና ማብ፤ ዘፀ15፥16 ይመ። የዘላለም ዝና፤ 55፥13 እና ማብ ይመ። ውሆችን ... ከፈለ፤ ዘፀ 14፥21፤ ከ11፥15፤ 51፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

[13]ፈረስ በምድረ በዳ እንደሚያልፍ ሁሉ፣
  እነርሱንም በጥልቁ ውስጥ አሳልፎ መራቸው፤
  ስለዚህም አልተሰናከሉም፤
[14]ወደ ሸለቆ እንደሚወርድ የከብት መንጋ፣
  *በእግዚአብሔር መንፈስ ዕረፍት ተሰጣቸው።*
ሕዝብህን በዚህ ሁኔታ የመራሃቸው፣
  ስምህን የከበረ ለማድረግ ነው።

[15]ከተቀደሰው፣ ከተከበረውና ከፍ ካለው
    ዙፋንህ፣
  ከሰማይ ወደ ታች ተመልከት፤
ኀይልህና ቅናትህ የት አለ?
  ገርነትህና ርኅራኄህ ከእኛ ርቀዋል።
[16]አብርሃም ባያውቀን፣
  እስራኤልም ባያስታውሰን እንኳ፣
አንተ እኮ አባታችን ነህ፤
  *እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ አባታችን ነህ፤
  ከጥንትም ቢሆን ስምህ "ቤዛችን" ነው።
[17]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከመንገድህ እንድንወጣ፣
  ልባችንን በማደንደን ለምን እንዳንፈራህ
    አደረግኸን?
ስለ ባሮችህ ስትል፣
  ስለ ርስትህ ነገዶች ስትል እባክህ ተመለስ።
[18]ለጥቂት ጊዜ ሕዝብህ የተቀደሰውን ስፍራ
    ወርሶ ነበር፤
  አሁን ግን ጠላቶቻችን መቅደስህን ረገጡት።
[19]እኛ እኮ ጥንትም የአንተው ነን፤
  እነርሱን ግን አንተ አላገዛሃቸውም፤
  በስምህም አልተጠሩም።[T]

# 64

አቤቱ፤ ሰማያትን ቀድደህ
    ምነው በወረድህ፤
  ምነዋ ተራሮች በፊትህ በተናወጡ፤
[2]እሳት ሲለኩስ ጭራሮን እንደሚያቀጣጥል፣
  ውሃንም እንደሚያፈላ፣
ስምህ በጠላቶችህ ዘንድ እንዲታወቅ ውረድ፤
  መንግሥታትም በፊትህ እንዲንቀጠቀጡ
    አድርግ።
[3]እኛ ያልጠበቅነውን አስፈሪ ነገር ባደረግህ
    ጊዜ፣
  አንተ ወረድህ፤ ተራሮችም በፊትህ ተንቀጠቀጡ።
[4]ከጥንት ጀምሮ፣
  በተስፋ ለሚጠባበቁት የሚደርስላቸው፣
እንደ አንተ ያለውን አምላክ ያየ ዐይን፣
  ያደመጠ ጆሮ ፈጽሞ አልነበረም።
[5]በደስታ ቅን ነገር የሚያደርጉትን፣
  መንገድህን የሚያስቡትንም ትረዳለህ፤
እኛ ግን በእነርሱ ላይ ሳናቋርጥ ኀጢአት
    በመሥራታችን፣
  እነሆ፣ ተቈጣህ፤
  ታዲያ እንዴት መዳን እንችላለን?
[6]ሁላችን እንደ ረከሰ ሰው ሆነናል፤
  የጽድቅ ሥራችን እንደ መርገም ጨርቅ ነው፤
ሁላችን እንደ ቅጠል ረግፈናል፤
  ኀጢአታችንም እንደ ነፋስ ጠራርጎናል።
[7]ማንም በጸሎት ስምህን አይጠራም፤
  አንተንም ለመያዝ የሚሞክር የለም፤
ፊትህን ከእኛ ሰውረሃል፤
  ስለ ኀጢአታችንም ትተኸናል።

[8]ይህም ሆኖ፣ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ
    አባታችን ነህ፤
  እኛ ሸክላዎች፣ አንተም ሸክላ ሠሪ ነህ፤
  ሁላችንም የእጅህ ሥራ ነን፤
[9]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከልክ በላይ አትቈጣን፤
  ኀጢአታችንንም ለዘላለም አታስብ፤
እባክህ ተለመነን፤ ፊትህን ወደ እኛ መልስ፤
  ሁላችንም የአንተ ሕዝብ ነንና።

63፥13 ዘፀ14፥22፤ ዘዳ32፥12፤ መዝ119፥11፤ ኤር31፥9
63፥14 ዘፀ33፥14፤ ዘዳ12፥9
63፥15 ዘፍ43፥31፤ ዘዳ26፥15፤1ነገ3፥26፤ 22፥19፤መዝ25፥6፤ 32፥1፤ኢሳ9፥7፤26፥11፤ 64፥12፤ሰቆ3፥50
63፥16 ዘፀ4፥22፤ ኢዮ14፥21፤ኢሳ41፥14፤ 44፥6፤59፥20፤ ኤር3፥4፤ዮሐ8፥41
63፥17 ዘፍ20፥13፤ ዘፀ4፥21፤34፥9፤ ዘኍ10፥36፤ኢሳ29፥13፤ ሰቆ3፥9
63፥18 ዘሌ26፥31፤ ዘዳ4፥26፤11፥17፤ 2ነገ25፥9፤ኢሳ28፥18፤ዳን8፥13፤ሉቃ21፥24
63፥19 ኢሳ43፥7፤ ኤር14፥9
64፥1 ቍ3፤ ዘፀ19፥18፤መዝ18፥9፤ 144፥5፤ሚክ1፥3
64፥2 መዝ99፥1፤ 119፥120፤ኢሳ30፥27፤ ኤር5፥22፤33፥9
64፥3 መዝ18፥7፤ 65፥5፤
64፥4 ኢሳ30፥18፤ 43፥10-11፤1ቆሮ2፥9
64፥5 ኢሳ10፥4፤ 26፥8
64፥6 ዘሌ5፥2፤ 12፥2፤መዝ1፥3:4፤ 90፥5-6፤ኢሳ46፥12፤ 48፥1፤ኤር4፥12
64፥7 ዘዳ31፥18፤ መዝ14፥4፤ኢሳ1፥15፤ 9፥18፤41፥28፤54፥8፤ 59፥4፤63፥5፤ኤር8፥6፤ ሕዝ22፥18-22፡30
64፥8 ዘፀ4፥22፤ ኢዮ10፥3፤ኢሳ19፥25፤29፥16፤ኤር3፥4፤ሮሜ9፥20-21
64፥9 መዝ100፥3፤ኢሳ43፥25፤51፥4፤54፥8፤57፥17፤60፥10፤ሰቆ5፥22

[T]19 *ወይም፣ አንተ እንዳልገዛሃቸው እንመስላለን፣ ልክ በአንተ ስም እንዳልተጠሩት*

63፥13 *በጥልቁ፤* በቀይ ባሕር ለማለት ነው (ዘፀ15፥5፡8፤ መዝ106፥9 ይመ)። ነገር ግን የዮርዳኖስንም ወንዝ የመሻገራቸው ነገር እዚህ ውስጥ ሳይካተት አልቀረም ቍ14 እና ማብ ይመ)።

63፥14 *ወደ ሸለቆ፤* የግጦሽ መሬትና ውሃ ለማግኘት ነው። *ዕረፍት ተሰጣቸው፤* በተስፋይቱ ምድር በከነዓን ርስት ተሰጣቸው (ዘዳ12፥9፤ ኢሱ1፥13፤ 21፥44 ይመ)።

63፥15 *ከፍ ካለው ዙፋንህ፤* 6፥1 ይመ። *ቅናትህ፤* 9፥7፤ 42፥13 እና ማብ ይመ። *ገርነትና ርኅራኄህ፤* ከሆሴ11፥8 ጋር ያነጻጽሩ። *ርቀዋል፤* 42፥14 እና ማብ ይመ።

63፥16 *አብርሃም ባያውቀን፤* ወላጅ አባት እንኳ ቢተው፣ እግዚአብሔር አይተውም (49፥14-15 እና ማብ ይመ)። *አባታችን፤* 64፥8፤ ዘዳ32፥6 ይመ። *ቤዛችን፤* 41፥14 እና ማብ ይመ።

63፥17 *ከመንገድህ እንድንወጣ፤* እስራኤላውያን መንገድ ሲስቱ (53፥6 ይመ) እግዚአብሔር በምድረ በዳ እንዲንከራተቱ አደረጋቸው። *ልባችንን በማደንደን፤* የሕዝቡ ልብ ደንድኖ ነበርና (6፥10፤ መዝ95፥8 ይመ)፤ እግዚአብሔርም ይህን አጽንቶታል (6፥10፤ ዘፀ4፥21 እና ማብ ይመ)። *ባሮችህ፤* እውነተኛ አማኞችን ማለት ነው (54፥17 እና ማብ ይመ)።

63፥18 *ጠላቶቻችን፤* ባቢሎናውያን ናቸው። *መቅደስህን ረገጡት፤* ሥዕላዊ በሆነ መንገድ በመዝ74፥3-7 ተገልጾአል፤ ከኢሳ64፥11 ጋር ያነጻጽሩ። የእግዚአብሔር ማደሪያ ስለ ሆነ ክብሩ አስጊ ሁኔታ ላይ ነበር (ከ48፥11 ጋር ያነጻጽሩ)።

63፥19 *በስምህም አልተጠሩም፤* 43፥7 እና ማብ ይመ።

64፥1 *ሰማያትን ቀድደህ፤* እዚህ ላይ ሰማይ ከድንኳን መጋረጃ ጋር ተነጻጽሮአል። ስለዚህና እንዲሁም እግዚአብሔር ለፍርድና ለትድግና በሚመጣበት ጊዜ በሰማይ ስለሚከሠተው ሁናቴ ተጨማሪውን ማብራሪያ በመሳ 5፥4-5፤ መዝ 18፥7-15፤ 144፥5፤ ናሆ1፥5፤ ዕን3፥3-7 ላይ ይመ።

64፥2 *ስምህ ... እንዲታወቅ፤* 30፥27 እና ማብ ይመ።

64፥3 *አስፈሪ ነገር፤* መዝ66፥3፡5-6 ይመ።

64፥4 *እንደ አንተ ያለውን አምላክ ... አልነበረም፤* 43፥11 እና ማብ ይመ። *በተስፋ ለሚጠባበቁት፤* 30፥18፤ 40፥31 እና ማብ ይመ።

64፥5 *ቅን ነገር የሚያደርጉትን፤* 56፥1 ይመ። *ተቈጣህ፤* 9፥12፡17፡21 እና ማብ ይመ። የእግዚአብሔር ቍጣ በስደቱ ወቅት ከፍተኛ ደረጃ ላይ ደርሶአል። *መዳን፤* 43፥3 እና ማብ ይመ።

64፥6 *እንደ ረከሰ፤* አስከፊ በሽታ ወይም ቍስል እንዳለበትና በሥርዐቱ መሠረት እንዳልነጻ ሰው ማለት ነው (6፥5፤ ዘሌ5፥2፤ 13፥45 ይመ)። *የጽድቅ ሥራችን፤* 57፥12 እና ማብ ይመ። *እንደ መርገም ጨርቅ፤* በአሪት ሥርዐት መሠረት ያልነጻች ሴት በወር አበባዋ ወቅት የምትጸዳዳበት ጨርቅ ነው (ዘሌ15፥19-24፤ ሕዝ36፥17 ይመ)። *እንደ ቅጠል ረግፈናል፤* በ1፥30 ላይም የተጠቀሰ ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው። *እንደ ነፋስ፤* ገለባን እንደሚያበንነው ለማለት ነው (17፥13፤40፥24 እና ማብ ይመ)።

64፥7 *ማንም ... ስምህን አይጠራም፤* በጭንቅና በመከራ ጊዜ እግዚአብሔር ከልብ የሚቀርብ ጸሎት ይፈልጋል (ለምሳሌ 2ዜና7፥14 ይመ)። *ፊትህን ከእኛ ሰውረሃል፤* 1፥15 እና ማብ ይመ።

64፥8 *አባታችን፤* 63፥16 እና ማብ ይመ። *ሸክላ ... ሠሪ፤* 45፥9 እና ማብ ይመ። *የእጅህ ሥራ፤* 60፥21 እና ማብ ይመ።

64፥9 *አትቈጣን፤* ይህን በ54፥7-8 ከተጠቀሰውና ቍጣውን ከሚያበርደው ቃል ኪዳን ጋር ያነጻጽሩ። *ኀጢአታችንንም ... አታስብ፤* 43፥25 እና ማብ ኤር31፥34 ሚክ7፥18 ይመ። *የአንተ ሕዝብ፤* 63፥17-19፤ መዝ79፥13 ይመ።

[10]የተቀደሱ ከተሞችህ ምድረ በዳ ሆኑ፤
ጽዮን ራሷ እንኳ ምድረ በዳ፣ ኢየሩሳሌምም
የተፈታች ሆናለች::
[11]አባቶቻችን አንተን ያመሰገኑበት የተቀደሰውና
የተከበረው ቤተ መቅደሳችን፣
በእሳት ተቃጥሎአል፤
ያማሩ ቦታዎቻችንም ሁሉ እንዳልነበር
ሆነዋል::
[12]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ይህ ሁሉ ሆኖ
አትመለስምን?
ዝም ብለህ ከልክ በላይ ትቀጣናለህን?

## ፍርድና ድነት

**65** “ሳልለምኑኝ ራሴን ገለጥሁላቸው፤
ሳልፈለጉኝ ተገኘሁላቸው::
ስሜን ሳልጠራ ሕዝብ፣
‘አለሁልህ፤ አለሁልህ’ አልሁት::
[2]ለዐመፀኛ ሕዝብ፣
መልካም ባልሆኑ መንገዶች ለሚሄዱ፣
የልባቸውን ምኞት ለሚከተሉ፣
ቀኑን ሙሉ እጆቼን ዘረጋሁ::
ዘወትር በፊቴ የሚያስቈጡኝ ሕዝቦች፣
[3]በአትክልት ቦታዎች መሥዋዕት የሚያቀርቡ፣
በሸክላ መሠዊያዎች ላይ ዕጣን የሚያጥኑ፣
ዘወትር በፊቴ የሚያስቈጡኝ ሕዝብ ናቸው፤
[4]በመቃብር መካከል የሚቀመጡ፣
በስውር ቦታዎች የሚያድሩ፣
የዕሪያ ሥጋ የሚበሉ፣
ማሰሮዎቻቸውን በረከሰ ሥጋ መረቅ
የሚሞሉ ናቸው፤
[5]‘ዘወር በል፤ አትቅረበኝ፤
አትጠጋኝ፤ እኔ ከአንተ ይልቅ ቅዱስ ነኝ’
የሚሉ ናቸው::
እንዲህ ያለው ሕዝብ በአፍንጫዬ ዘንድ እንደ
ጢስ፣
ቀኑን ሙሉ እንደሚነድድ እሳት ነው::
[6]“እነሆ፤ እንዲህ የሚል ተጽፎ በፊቴ ተቀምጦአል፤
ዝም አልልም፤ ነገር ግን እንደ ሥራው
እሰጠዋለሁ፤
የእጃቸውንም እከፍላቸዋለሁ፤
[7]የእናንተን ኀጢአት የአባቶቻችሁንም ኀጢአት
እበቀላለሁ”
ይላል *እግዚአብሔር*፡፡
“በተራሮች ላይ የሚቃጠል መሥዋዕት ስላቀረቡ፣
በኰረብቶች ላይ ስለ ሰደቡኝ፣
በሰፈሩት ቍና ይሰፈርባቸዋል፤
ስለ ቀደሙት ሥራዎቻቸውም የእጃቸውን
ያገኛሉ::”

[8]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
“በወይኑ ዘለላ ውስጥ ጭማቂው ገና እንዳለ
ሁሉ፣
ሰዎችም፣ ‘በውስጡ ጥሩ ነገር ስላለ
አትቍረጡት’ እንደሚሉ፣
እኔም ስለ ባሮች ስል እንዲሁ አደርጋለሁ፤
ሙሉ በሙሉ አላጠፋቸውም።
[9]ከያዕቆብ ዘር የሆኑትን፣
ከይሁዳም ተራሮቼን የሚወርሱትን
አመጣለሁ::
የተመረጠው ሕዝቤ ይወርሳቸዋል፤
ባሪያዎቼም በዚያ ይኖራሉ::
[10]አጥብቀው ለሚፈልጉኝ ሕዝቤ፣
ሳሮን የበጎች መሰማሪያ፣
የአኮር ሸለቆም የከብቶች ማረፊያ ይሆናል::
[11]“ነገር ግን እግዚአብሔርን ለተዋችሁት
ለእናንተ፣
የተቀደሰ ተራራዬን ለረሳችሁት፣
‘ዕጣ ፈንታ’ ለተባለ ባዕድ አምላክ ማዕድ ላዘጋጃችሁት፣

64፥10 ዘዳ29፥23፤ መዝ78፥54፤ ኢሳ1፥26
64፥11 ቍ10-11፤ ዘሌ26፥31፤2ነገ25፥9፤ መዝ74፥3-7፤ ሰቆ1፥7:10፤2፥7
64፥12 ዘፍ43፥31፤ አስ4፥14፤መዝ50፥21፤ 74፥10-11፤83፥1
65፥1 መዝ14፥4፤ ኢሳ43፥7፤ሆሴ1፥10፤ ሮሜ9፥24-26:30፤ 10፥20፤ኤፌ2፥12
65፥2 መዝ78፥8፤ 81፥11-12፤ምሳ24፥2፤ ኢሳ1፥2:23፤66፥18፤ ሮሜ10፥21
65፥3 ዘሌ2፥2፤ ኢዮ1፥11፤ኢሳ1፥29፤ ኤር41፥5፤44፥17፤ ሕዝ23፥41
65፥4 ዘሌ11፥7፤ 19፥31፤ኢሳ8፥19
65፥5 መዝ40፥4፤ ምሳ10፥26፤ ማቴ9፥11፤ሉቃ7፥39፤ 18፥9-12
65፥6 2ዜና6፥23፤ መዝ50፥3፤79፥12፤ ኢሳ59፥18፤ ኤር16፥18፤ሕዝ9፥10፤ ሉቃ6፥38
65፥7 ዘፀ20፥5፤ ምሳ10፥24፤ ኢሳ10፥12፤22፥14፤ 57፥7፤ኤር32፥18
65፥8 ኢሳ5፥2፤ 54፥17
65፥9 ዘኍ34፥13፤ ኢሳ14፥1፤32፥18፤ 45፥19፤60፥21፤ ኤር50፥19፤ አሞ9፥11-15
65፥10 ኢሱ7፥26፤ 1ዜና27፥29፤ ኢሳ35፥2፤51፥1፤ ኤር31፥12፤33፥12፤ ሕዝ34፥13-14፤ሐሥ9፥35
65፥11 ዘዳ28፥20፤ 29፥24-25፤32፥15፤ 33፥19፤መዝ137፥5፤ኢሳ1፥28፤5፥22፤ኤር2፥13፤19፥4

64፥10 *የተቀደሱ ከተሞችህ፤* እስራኤል ቅድስት አገር ነች (መዝ78፥54)፤ ኢየሩሳሌም አብዛኛውን ጊዜ፣ “ቅድስት ከተማ” ተብላ ትጠራለች (48፥2 እና ማብ ይመ):: *ጽዮን ራሷ እንኳ ምድረ በዳ … የተፈታች፤* 1፥7-9 እና ማብ ይመ::

64፥11 *የተቀደሰውና የተከበረው ቤተ መቅደሳችን፤* 60፥7 እና ማብ 63፥15 ይመ:: *በእሳት ተቃጥሎአል፤* የኢሳይያስ ሰቆቃ እዚህ ላይ ከፍተኛ ደረጃ ላይ ይደርሳል፤ 63፥18 እና ማብ ይመ::

64፥12 *አትመለስምን? ዝም ብለህ፤* 42፥14፤ 57፥11፤ 62፥1:6-7 እና ማብ ይመ::

*65፥1-66፥24፤* ም 58-66፣ ም 40-66 እና ለጠቅላላው መጽሐፍ የተሰጠ ትልቁ መደምደሚያ ነው::

65፥1 *ሳልለምኑኝ … ሳልፈለጉኝ፤* እግዚአብሔር እዚህ ላይ የኢሳይያስን ጸሎትና ልመና እየተቀበለ ነው፤ እስራኤላውያን እግዚአብሔርን ቢፈልጉትም፣ ከዐንገት በላይ እንጂ እንደሚገባ ከእርሱ ጋር ተጣብቀው መኖር አልቻሉም (55፥6፤ 58፥2 እና ማብ ይመ):: *ስሜን ሳልጠራ፤* 64፥7 ይመ:: *አለሁልህ አልሁት፤* 58፥9 ይመ::

65፥2 *ለዐመፀኛ ሕዝብ፤* 1፥2፤ 30፥1:9 እና ማብ ይመ:: *የልባቸውን ምኞት፤* 59፥7 እና ማብ ይመ::

65፥3 *በአትክልት ቦታዎች፤* 1፥29 እና ማብ ይመ:: *ዕጣን የሚያጥኑ፤* የሰማይ ንግሥት ብለው ስም ያወጡላትን በሚያመልኩበት ጊዜ ነው (ኤር44፥17-19 ይመ):: *በፊቴ፤* በድፍረት ተሞልተው ማለት ነው (ከ3፥8-9 ጋር ያነጻጽሩ):: *የሚያስቈጡኝ፤* ጣዖትን በማምለክ ማለት ነው (መሳ2፥12-13 ይመ)::

65፥4 *በመቃብር መካከል የሚቀመጡ፤* ምናልባት የሙታንን መንፈስ ጠርቶ ለማነጋገር ይሆናል (8፥19 እና ማብ፤ 57፥9፤ ዘዳ18፥11 ይመ):: *የዕሪያ ሥጋ፤* በአሪቱ ሥርዐት መሠረት ርኩስ ነው ተብሎ ስለሚታመን ነው (66፥3:17፤ ዘሌ11፥7-8 ይመ)::

65፥5 *እኔ … ቅዱስ ነኝ፤* የአምልኮ ጣዖትን ሥርዐት ሥራዬ ብለው የሚከታተሉ ወገኖች ራሳቸውን ከሌላው በላይ አድርገው ይቈጥራሉ (በማቴ9፥11፤ ሉቃ7፥39፤ 18፥9-12 ላይ ፈሪሳውያን ከሚያደርጉት መመጻደቅ ጋር ይህን ያነጻጽሩ)::

65፥6 *ዝም አልልም፤* የ64፥12 ምላሽ ነው:: *የእጃቸውንም እከፍላለሁ፤* 59፥18 እና ማብ ይመ::

65፥7 *በተራሮች ላይ የሚቃጠል መሥዋዕት፤* በየተራራው ላይ በኣል ለተባለው ጣዖት የሚቀርበውን መሥዋዕት የሚያመለክት ነው (57፥7፤ ሆሴ2፥13 ይመ):: *ስለ ሰደቡኝ፤* ሕዝ20፥27-28 ይመ::

65፥8 *ዘለላ፤* እስራኤል መራራ የወይን ፍሬ ያፈራች የአትክልት ቦታ ሆና ተገኝታለች (5፥2:4:7):: *ባሮቼ፤* ቍ9፤13-15፤ 54፥17 እና ማብ ይመ)::

65፥9 *ከያዕቆብ … ከይሁዳም፤* የሰሜኑንና የደቡቡን መንግሥት የሚያመለክት ነው:: *ዘር፤* ኤር31፥36 ይመ:: *ተራሮቼን የሚወርሱትን፤* 49፥8፤ 60፥21 እና ማብ ይመ:: አብዛኛው መሬት ተራራማ ስለ ሆነ (መሳ1፥9፤ ሕዝ6፥2-3 ይመ)፣ “ተራሮች” ሲል አገሩን በሙሉ ማመልከቱ ነው:: *የተመረጠው ሕዝቤ፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ:: *ይወርሳቸዋል፤* 57፥13 እና ማብ ይመ::

65፥10 *አጥብቀው ለሚፈልጉኝ፤* ቍ1:51፥1 እና ማብ ይመ:: *ሳሮን፤* 33፥9 እና ማብ ይመ:: *የአኮር ሸለቆም፤* ከኢያሪኮ አጠገብ ያለ ሸለቆ ነው (ኢሱ7፥24:26፤ ሆሴ2፥15 ይመ):: ሳሮንና አኮር ከምድሪቱ ምዕራብና ምሥራቅ ጫፍ ላይ ስለሚገኙ፣ ምናልባት በአጠቃላይ አገሩን በሙሉ ሳይወክሉ አይቀሩም::

65፥11 *እግዚአብሔርን ለተዋችሁት፤* 1፥4 ይመ:: *የተቀደሰ ተራራዬን፤* 2፥2-4 እና ማብ ይመ:: *ዕጣ ፈንታ … ዕድል፤* የመልካም

‘ዕድል’ ለተባለም ጣዖት ድብልቅ የወይን
ጠጅ በዋንጫ ለሞላችሁት፣
[12]ተጣርቼ ስላልመለሳችሁ፣
ተናግሬ ስላልሰማችሁ፣
በፊቴ ክፉ ነገር ስላደረጋችሁ፣
የሚያስከፋኝን ነገር ስለ መረጣችሁ፣
ለሰይፍ እዳርጋችኋለሁ፤
ሁላችሁም ለመታረድ ትጐነበሳላችሁ::”
[13]ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“ባሮቼ ይበላሉ፤
እናንተ ግን ትራባላችሁ፤
ባሮቼ ይጠጣሉ፤
እናንተ ግን ትጠማላችሁ፤
ባሮቼ ደስ ይላቸዋል፤
እናንተ ግን ታፍራላችሁ::
[14]ባሮቼ፣
ከልብ በመነጨ ደስታ ይዘምራሉ፤
እናንተ ግን፣
ልባችሁ በማዘኑ ትጮኻላችሁ፤
መንፈሳችሁ በመሰበሩም ወዮ ትላላችሁ::
[15]ስማችሁንም፣
የተመረጠው ሕዝቤ ርግማን እንዲያደርገው
ትተዋላችሁ፤
ጌታእግዚአብሔር ይገድላችኋል፤
ለአገልጋዮቹ ግን ሌላ ስም ይሰጣቸዋል::
[16]ስለዚህ በምድሪቱ ላይ በረከትን የሚጠራ፣
በእውነት አምላክ ስም ይባረካል፤
በምድሪቱ መሐላን የሚምል፣
በእውነት አምላክ ስም ይምላል፤
ያለፉት ችግሮች ተረስተዋል፤
ከዐይኖቼም ተሰውረዋል::

## አዲስ ሰማያትና አዲስ ምድር

[17]“እነሆ፤ እኔ፣
አዲስ ሰማያትንና አዲስ ምድርን እፈጥራለሁ፤
ያለፉት ነገሮች አይታሰቡም፤
አይታወሱም::
[18]ነገር ግን በምፈጥረው፣
ደስ ይበላችሁ፤ ለዘላለም ሐሤት አድርጉ::
ኢየሩሳሌምን ለደስታ፣
ሕዝቧን ለሐሤት እፈጥራለሁና::
[19]በኢየሩሳሌም እደሰታለሁ፤
በሕዝቤ ሐሤት አደርጋለሁ፤
የልቅሶና የጩኸት ድምፅ፣
ከእንግዲህ በዚያ አይሰማም::
[20]“ከእንግዲህም በዚያ፣
ለጥቂት ጊዜ ብቻ በሕይወት የሚኖር ሕፃን፣
ወይም ዕድሜ ያልጠገበ አረጋዊ አይኖርም፤
አንድ መቶ ዓመት የሞላው ሰው ቢሞት፣
በአጭር እንደ ተቀጨ ይቈጠራል፤
አንድ ሰው መቶ ዓመት ሳይሞላው ቢሞት፣
እንደ ተቀሠፈ ይገመታል::
[21]ሰዎች ቤት ይሠራሉ፤ በውስጡም ይኖራሉ፤
ወይንን ይተክላሉ፤ ፍሬውንም ይበላሉ::
[22]ከእንግዲህ ለሌሎች መኖሪያ ቤት አይሠሩም፤
ወይም ሌላው እንዲበላው አይተክሉም፤
የሕዝቤ ዕድሜ፣
እንደ ዛፍ ዕድሜ ይረዝማል፤
እኔ የመረጥኋቸው፣
በእጃቸው ሥራ ለረጅም ዘመን ደስ ይላቸዋል::
[23]ድካማቸው በከንቱ አይቀርም፤
ዕድለ ቢስ ልጆችም አይወልዱም፤
እነርሱና ዘራቸው፣
እግዚአብሔር የባረከው ሕዝብ ይሆናሉ::
[24]ገና ሳይጣሩ እመልስላቸዋለሁ፤
ተናግረው ሳይጨርሱ እሰማለሁ::

65፥12 2ዜና36፥15-16፤ መዝ149፥7፤ ምሳ1፥24-25፤ ኢሳ1፥20:24፤27፥1፤ 30፥25፤41፥28፤66፥4፤ ኤር7፥13:27፤13፥11፤ 25፥3፤26፥5፤ሚክ5፥15
65፥13 ኢዮ18፥12፤ ኢሳ1፥19፤3፥1፤33፥16፤ 41፥17፤44፥9፤60፥5፤ 61፥7፤ሉቃ6፥25
65፥14 መዝ109፥28፤ ኢሳ15፥2፤ ሰቆ3፥14-20፤ ማቴ8፥12፤ ሉቃ13፥28፤ያዕ5፥13
65፥15 ዘፍ32፥28፤ ዘኍ5፥27፤ መዝ102፥8፤ራእ2፥17
65፥16 ዘዳ29፥19፤ ኢዮ11፥16፤መዝ31፥5፤ 63፥11፤ኢሳ19፥18፤ ራእ3፥14
65፥17 ኢሳ41፥22፤ 43፥18፤66፥22፤ ኤር3፥16፤2ቆሮ5፥17፤ 2ጴጥ3፥13፤ራእ7፥17
65፥18 ዘዳ32፥43፤ መዝ98፥1-9፤ ኢሳ25፥9፤ራእ21፥2
65፥19 ዘዳ30፥9፤ ኢሳ25፥8፤35፥10፤ 62፥5፤ራእ7፥17
65፥20 ዘፍ5፥1-32፤ 15፥15፤መክ8፥13፤ ኢሳ11፥8፤ዘካ8፥4
65፥21 2ነገ19፥29፤ ኢሳ32፥18፤37፥30፤ 61፥4፤ሕዝ28፥26፤ አሞ9፥14
65፥22 ዘዳ28፥30፤ መዝ1፥3፤21፥4፤ 91፥16፤92፥12-14፤ ኢሳ14፥1
65፥23 ዘፍ12፥2፤ ዘዳ28፥3-12:32:41፤ ኢሳ44፥3፤49፥4፤ኤር16፥3-4፤ሐዋ2፥39፤1ቆሮ15፥58
65፥24 ኢዮ8፥6፤ኢሳ30፥19፤55፥6፤ዳን9፥20-23፤10፥12፤ ዘካ10፥6፤ማቴ6፥8

ነገር አጋጣሚና የዕድል አማልክት ናቸው ተብለው የሚታመኑባቸውን ያመለክታል፤ ኢሱ11፥17 ይመ:: *በታ ላዘጋጃችሁት … ድብልቅ የወይን ጠጅ፤* ለአማልክት የሚቀርበውን የምግብና የመጠጥ ቍርባን የሚያመለክት ነው፤ የ5፥22 ማብ ይመ፤ ከቍ3፤ ኤር7፥18 ጋር ያነጻጽሩ::

65፥12 *ተጣርቼ ስላልመለሳችሁ፤* 50፥2 እና ማብ 2ዜና36፥15-16 ይመ:: *የሚያስከፋኝን ነገር ስለ መረጣችሁ፤* በ56፥4 ላይ የተገለጹት ጃንደረባዎች የነበራቸውን ታማኝነት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ:: የቍ12 የመጨረሻዎቹ አራት ስንኞች በ66፥4 ላይ ከተገለጹት ጋር እጅግ ተመሳሳይ ናቸው:: *ለሰይፍ፤* እንደ ኤዶም ላሉት የእግዚአብሔር ጠላቶች የተዘጋጀ ነው (34፥5-6)፤ የእስራኤል ምድር ያበቀለቻቸው ክፉዎችም እንዲሁ በሰይፍ ይቀጣሉ (1፥20፤ 59፥18 እና ማብ 66፥16 ይመ)::

65፥13 *ይበላሉ … ይጠጣሉ፤* 41፥17-18፤ 49፥10 ይመ:: *ትራባላችሁ … ትጠማላችሁ፤* 5፥13፤ 8፥21 ይመ:: *ደስ ይላቸዋል፤* 61፥7 እና ማብ 66፥14 ይመ:: *ታፍራላችሁ፤* 42፥17፤ 44፥9:11 ይመ::

65፥14 *ደስታ ይዘምራሉ፤* 35፥10፤ 54፥1 እና ማብ ይመ:: *መንፈሳችሁ በመሰበሩም፤* የእግዚአብሔርን ፈውስ ባለመፈለጋቸው ነው፤ 61፥1 እና ማብ ይመ::

65፥15 *የተመረጠው ሕዝቤ፤* ቍ9 እና ማብ ይመ:: *ርግማን፤* ስለ ርግማን ሲታሰብ ዐመፀኞች እስራኤላውያን ምሳሌና መተረቻ ይሆናሉ (ኤር29፥22):: *ሌላ ስም፤* ምናልባትም በ62፥2 ላይ የተጠቀሰውን አዲስ ስም ለማለት ይሆናል፤ የዚያኑ ማብ ይመ::

65፥16 *በረከትን የሚጠራ፤* 48፥1፤ ዘዳ29፥19 ይመ:: *በእውነት አምላክ፤* እግዚአብሔር በቃል ኪዳኑ እውነተኛና ታማኝ ነው:: እውነት የሚለውን ቃል ዕብራይስጡ፣ “አሜን” ይለዋል (2ቆሮ1፥20 ይመ፤ ከራእ3፥14 ጋር ያነጻጽሩ):: *መሐላን የሚምል፤* 45፥23 ይመ፤ ምናልባት በበአል ስም ከሚምሉት (ኤር12፥16) ጋር ተነጻጽሮ ይሆናል::

65፥17 *አዲስ ሰማያትንና አዲስ ምድርን፤* ትንቢተ ኢሳይያስ አዳዲስ ነገሮች በከፍተኛ ደረጃ የሚገለጡበት ነው (42፥9፤ 48፥6 እና ማብ ይመ):: *ያለፉት ነገሮች፤* ያለፈውን ሥርዐት ነገሮች (ራእ 21፥4)፣ ሥቃይንና ሐዘንንም ጨምሮ ማለት ነው::

65፥18 *ደስ ይበላችሁ … ሐሤት አድርጉ፤* 66፥10፤51፥3 እና ማብ ይመ:: *ኢየሩሳሌምን … እፈጥራለሁና፤* ሐዋርያው ዮሐንስ፣ አዲሱን ሰማይና አዲሱን ምድር የሚገልጸውን ሐሳብ “ከአዲሲቷ ኢየሩሳሌም” መምጣት ጋር አያይዞታል (ራእ21፥1-2):: ከምርኮ መልስ የተሠራችው ኢየሩሳሌምና የመሲሑ መንግሥት ወደ ታላቂቱ ኢየሩሳሌም ያመለክታሉ (የ54፥11-12 ማብ ይመ)::

65፥19 *እደሰታለሁ … ሐሤት አደርጋለሁ፤* 62፥4-5 እና ማብ ይመ:: *የልቅሶና የጩኸት ድምፅ፤* 25፥8 እና ማብ 35፥10 ይመ::

*65፥20-25፤* 11፥6-9 እና ማብ ይመ::

65፥20 *መቶ ዓመት … በአጭር እንደ ተቀጨ፤* አዳምና ትውልዱ ከኖሩበት ዘመን ጋር ይወዳደራል፤ የዘፍ 5 የትውልድ ሐረግ ይመ፤ ይሁን እንጂ ዘፍ5፥5 ይመ::

*65፥21-22፤* ይህን ሙሴ በዘዳ28፥30 ላይ ስለ እንቢተኞች ከተናገረው ጋር ያነጻጽሩ::

65፥21 *ወይንን ይተክላሉ፤* 62፥8-9 ይመ::

65፥22 *እንደ ዛፍ ዕድሜ፤* በመዝ1፥3፤ 92፥12-14 ከተጠቀሱት ጻድቃን ጋር ይነጻጸራል:: *የመረጥኋቸው፤* 41፥8-9 እና ማብ ይመ:: *ለረጅም ዘመን ደስ ይላቸዋል፤* ከመዝ91፥16 ጋር ያነጻጽሩ::

65፥23 *ድካማቸው በከንቱ አይቀርም፤* 49፥4 እና ማብ ይመ:: *ዕድለ ቢስ፤* እንደ ሞትና እንደ ምርኮ ዐይነቱን ነገር ማለት ነው:: *እግዚአብሔር የባረከው ሕዝብ፤* 61፥9 እና ማብ ይመ::

65፥24 *ሳይጣሩ እመልስላቸዋለሁ፤* 30፥19፤ 58፥9፤ ማቴ6፥8 ይመ::

²⁵ተኵላና የበግ ጠቦት በአንድነት ይበላሉ፤
አንበሳ እንደ በሬ ሣር ይበላል፤
እባብ ትቢያ ይልሳል፤
በተቀደሰው ተራራዬም፣
ጒዳት አያደርሱም፤ ጥፋት አያመጡም፤”
ይላል እግዚአብሔር።

## ፍርድና ተስፋ

**66** እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“ሰማይ ዙፋኔ ነው፤
ምድርም የእግሬ ማረፊያ ናት፤
ታዲያ የምትሠሩልኝ ቤት፣
የማርፍበትስ ስፍራ የቱ ነው?
²እነዚህን ነገሮች ሁሉ እጄ አልሠራችምን?
እንዲኖሩስ ያደረግሁ እኔ አይደለሁምን?”
ይላል እግዚአብሔር።
“ነገር ግን እኔ ወደዚህ፣
ትሑት ወደ ሆነና መንፈሱ ወደ ተሰበረ፣
በቃሌም ወደሚንቀጠቀጥ ሰው እመለከታለሁ።
³ነገር ግን ወይፈን የሚሰዋልኝ፣
ሰው እንደሚገድል ነው፤
የበግ ጠቦት የሚያቀርብልኝ፣
የውሻ ዐንገት እንደሚሰብር ሰው ነው፤
የእህል ቍርባን የሚያዘጋጅልኝ፣
የዕሪያ ደም እንደሚያቀርብልኝ ሰው ነው፤
የመታሰቢያን ዕጣን የሚያጥንልኝም፣
ጣዖትን እንደሚያመልክ ሰው ነው፤
የገዛ መንገዳቸውን መርጠዋል፤
ነፍሳቸውም በርኵሰታቸው ደስ ይላታል።
⁴ስለዚህ ችግር እንዲደርስባቸው አደርጋለሁ፤
የፈሩትንም አመጣባቸዋለሁ፤
በተጣራሁ ጊዜ የመለሰ፣
በተናገርሁ ጊዜ ያደመጠ ሰው የለምና።
በፊቴ ክፉ ነገር አደረጉ፤
የሚያስከፋኝንም መረጡ።”
⁵እናንት በቃሉ የምትንቀጠቀጡ፣
ይህን የእግዚአብሔር ቃል ስሙ፤
“እናንት ወንድሞቻችሁ የጠሏችሁ፣
ስለ ስሜም አውጥተው የጣሏችሁ፣
‘እስቲ እግዚአብሔር ይክበርና፣
የእናንተን ደስታ እንይ’ አሏችሁ፤
ይሁን እንጂ ማፈራቸው አይቀርም።
⁶ያን የጩኸት ድምፅ ከከተማው ስሙ!
ያን ጫጫታ ከቤተ መቅደሱ ስሙ!
ይኸውም የእግዚአብሔር ድምፅ ነው፤
ለጠላቶቹም የሚገባቸውን ሁሉ ይከፍላቸዋል።
⁷“ከማማጧ በፊት፣
ትወልዳለች፤
በምጥ ጣር ከመያዟ በፊት፣
ወንድ ልጅ ትገላገላለች።
⁸እንዲህ ያለ ነገር ማን ሰምቶ ያውቃል?
እንዲህ ያለ ነገርስ ማን አይቶ ያውቃል?
አገር በአንድ ጀምበር ይፈጠራልን?
ወይስ ሕዝብ በቅጽበት ይገኛል?
ጽዮንን ምጥ ገና ሲጀምራት፣
ልጆቿን ወዲያውኑ ትወልዳለች።
⁹ሊወለድ የተቃረበውን፣
እንዳይወለድ አደርጋለሁን?” ይላል
እግዚአብሔር።
“በሚገላገሉበት ጊዜስ፣
ማሕፀን እዘጋለሁን?” ይላል አምላክሽ።
¹⁰“ወዳጆቿ የሆናችሁ ሁሉ፣
ከኢየሩሳሌም ጋር ደስ ይበላችሁ፤
ስለ እርሷም ሐሤት አድርጉ፤
ለእርሷ ያለቀሳችሁ ሁሉ፣
ከእርሷ ጋር እጅግ ደስ ይበላችሁ።
¹¹ከሚያጽናኑ ጡቶቿ፣
ትጠባላችሁ፤ ትረካላችሁም፤
እስክትረኩም ትጠጣላችሁ፤
በተትረፈረፈ ሀብቷም ትደሰታላችሁ።
¹²እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“እነሆ ሰላምን እንደ ወንዝ ውሃ አፈስላታለሁ፤
የመንግሥታትንም ብልጽግና እንደ ጅረት ውሃ
አጐርፍላታለሁ፤
ትጠባላችሁ፤ በዕቅፏም ትያዛላችሁ፤
በጒልበቷም ላይ ትፈነድቃላችሁ።
¹³እናት ልጇን እሹሩሩ እንደምትል፣
እኔም እናንተን እሹሩሩ እላችኋለሁ፤

65፥25 ዘፍ3፥14፤ ኢዮ5፥23፤40፥15፤ ኢሳ2፥4፤11፥6፤ ሚክ7፥17
66፥1 2ሳሙ7፥7፤ 1ነገ8፥27፤2ዜና6፥18፤ መዝ2፥4፤9፥7፤ ማቴ5፥34-35፤23፥22፤ ዮሐ4፥20-21፤ ሐሥ7፥49፤17፥24
66፥2 ዕዝ9፥4፤ ኢሳ40፥26፤57፥15፤ ማቴ5፥3-4፤ ሉቃ18፥13-14፤ ሐሥ7፥50፤17፥24
66፥3 ቍ17፤ ዘሌ2፥2፤11፥7፤ ዘዳ27፥15፤ ኢሳ1፥11፤57፥17፤ ሕዝ8፥9-13
66፥4 1ሳሙ8፥19፤ 2ነገ21፥2፡4፡6፤ ምሳ10፥24፤ኢሳ10፥12፤ 41፥28፤59፥12፤65፥12
66፥5 ዕዝ9፥4፤ መዝ38፥20፤ኢሳ44፥9፤ 60፥15፤ ሉቃ13፥17፤ ዮሐ15፥21
66፥6 ዘሌ26፥28፤ 1ሳሙ2፥10፤ መዝ68፥33፤ኢሳ65፥6፤ ኢዩ3፥7
66፥7 ኢሳ54፥1፤ ራእ12፥5
66፥8 ኢሳ49፥20፡21፤64፥4፤ኤር18፥13
66፥9 ኢሳ37፥3
66፥10 ዘዳ32፥43፤ መዝ26፥8፤ኢሳ25፥9፤ 57፥19፤61፥2፤ ሮሜ15፥10
66፥11 ዘፍ49፥25፤ ዘኍ11፥12፤25፥1፤ ኢሳ25፥6፤60፥16
66፥12 ዘኍ11፥12፤ መዝ72፥3፤119፥165፤ ኢሳ9፥6፤33፥21፤ 60፥4፡5፤61፥6
66፥13 ኢሳ40፥1፤ 49፥15፤2ቆሮ1፥4፤ 1ተሰ2፥7

65፥25 *ተኵላና የበግ ጠቦት … አንበሳ፤* 11፥6-9 እና ማብ ይመ። እባብም ቢሆን ጒዳት የሚያደርስ አይሆንም (11፥8 ይመ)።

66፥1 *ዙፋኔ … የእግሬ ማረፊያ፤* 40፥22 እና ማብ ይመ። *የምትሠሩልኝ ቤት … የቱ ነው?* የቱን ያህል ውብና ታላቅ ቢሆንም እንኳ፣ እግዚአብሔር በሰው እጅ በተሠራ ቤተ መቅደስ እንደማይወሰን ሰሎሞን ተገንዝቦ ነበር (1ነገ8፥27)።

66፥2 *እነዚህን ነገሮች ሁሉ እጄ አልሠራምን?* 40፥26 እና ማብ ይመ። *ትሑት ወደ ሆነና መንፈሱ ወደ ተሰበረ፤* 57፥15 እና ማብ ይመ።

*66፥3፤* ኢሳይያስ ተቀባይነት ስለ ሌለው መሥዋዕት በ1፥11-14 ላይ የተናገረውን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ። *የውሻ ዐንገት እንደሚሰብር፤* ውሻ ርኩስ ስለ ሆነ ለመሥዋዕት አይቀርብም። የአህያን ዐንገት ስለ መስበር በዘፀ13፥13 ላይ የተነገረውን ሕግ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ። *የዕሪያ ደም፤* 65፥4 እና ማብ ይመ። ውሻና ዕሪያ በማቴ7፥6፤ በ2ጴጥ2፥22 ላይ በአንድነት ተጠቅሰዋል። *ጣዖትን እንደሚያመልክ፤* 44፥19 እና ማብ ይመ። *በርኵሰታቸው፤* ምናልባትም ጣዖቶችን የሚመለከት ሳይሆን አይቀርም (ኤር4፥1 ይመ)።

66፥4 *ችግር እንዲደርስባቸው አደርጋለሁ፤* ከ65፥7 ጋር ያነጻጽሩ። *የሚያስከፋኝንም፤* ስለ እነዚህ አራት ስንኞች 65፥12 እና ማብ ይመ።

66፥5 *የምትንቀጠቀጡ፤* ቍ2 ይመ። *ወንድሞቻችሁ፤* እስራኤላውያን ወገኖቻቸውን ለማመልከት ነው (ሐሥ22፥1 ይመ)። *ደስታ፤* በምፀት የተገለጠ አባባል ነው፤ 5፥19፤ መዝ22፥8 ይመ።

66፥6 *ከከተማው፤* ምናልባትም ኢየሩሳሌምን ነው። *ለጠላቶቹም የሚገባቸውን ሁሉ ይከፍላቸዋል፤* 59፥18 እና ማብ ይመ 65፥6-7።

66፥7 *ከማማጧ በፊት፤* ጽዮን እንዴት መካን እንደ ሆነች 54፥1 እና ማብ ይመ።

66፥8 *አገር በአንድ ጀምበር፤* 49፥19-20 እና ማብ ይመ።

66፥9 *ሊወለድ የተቃረበውን፤* 37፥3 እና ማብ ይመ።

66፥10 *ወዳጆቿ የሆናችሁ ሁሉ፤* ከመዝ137፥6 ጋር ያነጻጽሩ። *ደስ ይበላችሁ፤ … ሐሤት አድርጉ፤* 65፥18 እና ማብ ይመ። *ያለቀሳችሁ ሁሉ፤* 57፥19፤ 61፥2 እና ማብ ይመ።

66፥11 *ትጠባላችሁ፤ ትረካላችሁም፤* በ60፥16 ኢየሩሳሌም የመንግሥታትን ወተት እንደምትጠጣ ተገልጾአል (የዚያኑ ማብ ይመ)፤ እዚህ ላይ ደግሞ እናት ሆና ቀርባለች (ከቍ12፤ 49፥23 ጋር ያነጻጽሩ)።

66፥12 *ሰላምን እንደ ወንዝ፤* 48፥18 እና ማብ ይመ። *የመንግሥታትንም ብልጽግና፤* 60፥5 እና ማብ ይመ። *እንደ ጅረት ውሃ፤* ይህን በ8፥7-8 ከተገለጠው አውዳሚ ውሃ ጋር ያነጻጽሩ፤ የዚያኑ ማብ ይመ። *በዕቅፏም፤* 40፥11 ይመ።

በኢየሩሳሌምም ትጽናናላችሁ።

[14]ይህን ስታዩ፣ ልባችሁ ሐሤት ያደርጋል፤
ዐጥንቶቻችሁም እንደ ሣር ይለመልማሉ፤
*የእግዚአብሔር* እጅ ከባሮቹ ጋር መሆኑ
ይታወቃል፤
ቍጣው ግን በጠላቶቹ ላይ ይገለጣል።
[15]እነሆ፤ *እግዚአብሔር* በእሳት ነበልባል ይመጣል፤
ሠረገሎቹም እንደ ዐውሎ ነፋስ ናቸው፤
ንዴቱን በቍጣ፣
ተግሣጹንም በእሳት ነበልባል ይገልጣል።
[16]በእሳትና በሰይፍ፣
*እግዚአብሔር* ፍርዱን በሰው ሁሉ ላይ ያመጣል፤
በ*እግዚአብሔር* ሰይፍ የሚታረዱት ብዙ
ይሆናሉ።

[17]"ወደ አትክልት ቦታዎች ለመሄድና ከተከሉቹ አንዱን ለማምለክ ራሳቸውን የሚቀድሱና የሚያነጹ፣ የዕሪያዎችንና የዐይጦችን ሥጋ፣ የረከሱ ነገሮችንም የሚበሉ ሁሉ የመጨረሻ ፍርዳቸውን በአንድነት ይቀበላሉ" ይላል *እግዚአብሔር*።

[18]"እኔም ሥራቸውንና ሐሳባቸውን ስለ ማውቅ፣ መንግሥታትንና ልሳናትን ሁሉ ልሰበስብ እመጣለሁ፤[u] እነርሱም መጥተው ክብሬንም ያያሉ።

[19]"በመካከላቸው ምልክት አደርጋለሁ፤ ከእነርሱም የተረፉትን አንዳንዶቹን ወደ አሕዛብ ወደ ተርሴስ፣ ወደ ፉጥ፣ ወደ ታወቁት ቀስተኞች ወደ ሉድ፣ ወደ ቶባልና ያዋን እንዲሁም ዝናዬን ወዳልሰሙትና ክብሬን ወዳላዩት ራቅ ወዳሉት ደሴቶች እልካቸዋለሁ፤ በሕዝቦችም መካከል ክብሬን ይናገራሉ። [20]ለ*እግዚአብሔር* ቍርባን እንዲሆኑ ወንድሞቻችሁን ሁሉ ከየመንግሥታቱ ወደ ተቀደሰው ተራራዬ ወደ ኢየሩሳሌም በፈረስ፣ በሠረገላና በጋሪ፣ በበቅሎና በግመል ያመጧቸዋል" ይላል *እግዚአብሔር*። "እስራኤላውያን የእህል ቍርባናቸውን በሥርዐቱ መሠረት በንጹ ዕቃዎች ወደ *እግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ እንደሚያቀርቡ እነዚህንም ያቀርቧቸዋል። [21]እኔም ካህናትና ሌዋውያን ይሆኑ ዘንድ አንዳንዶቹን እመርጣቸዋለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*።

[22]"እኔ የምሠራቸው አዲስ ሰማያትና አዲስ ምድር በፊቴ ጸንተው እንደሚኖሩ፣ የእናንተና የዘራችሁ ስም እንደዚሁ ጸንቶ ይኖራል" ይላል *እግዚአብሔር*፤ [23]"ከአንዱ ወር መባቻ እስከ ሌላው፣ እንዲሁም ከአንዱ ሰንበት እስከ ሌላው፣ የሰው ልጅ ሁሉ በፊቴ ሊሰግድ ይመጣል" ይላል *እግዚአብሔር*፤ [24]"ወጥተውም በእኔ ላይ ያመፁትን ሰዎች ሬሳ ያያሉ፤ ትላቸው አይሞትም፤ እሳታቸው አይጠፋም፤ ለሰውም ዘር ሁሉ አስጸያፊ ይሆናሉ።"

66፥14 ዕዝ5፥5፤ መዝ72፥16፤ ኢሳ10፥5፤ 25፥9፤ 30፥27፤ 41፥20፤ 54፥17፤ 60፥5፤ ሕዝ2፥23
66፥15 ዘዳ28፥20፤ 2ነገ2፥1፡11፤ መዝ9፥5፤ 39፥11፤ 68፥17፤ ኢሳ1፥31፤ 42፥25
66፥16 ኢሳ1፥20፤ 10፥4፤ 13፥9፡11፤ 27፥1፤ 30፥30፤ ኤር2፥35፤ ሕዝ14፥21፤ 36፥5፤ አሞ7፥4፤ ሚል4፥1
66፥17 ዘሌ11፥7፡29፤ መዝ37፥20፤ ኢሳ1፥28፡ 29
66፥18 ዘፀ16፥7፤ ምሳ24፥2፤ ኢሳ2፥3፤ 59፥19፤ 65፥2፤ ዘካ12፥3
66፥19 ዘፍ10፥2፤ 2ነገ19፥31፤ 1ዜና16፥24፤ ኢሳ2፥16፤ 11፥10፡11፤ 24፥15፤ 49፥22፤ ኤር31፥10፤ 46፥9፤ ሕዝ27፥10፤ ዳን11፥18፤ ማቴ24፥30
66፥20 ዘዳ33፥19፤ ዕዝ2፥66፤ ኢሳ2፥2፤ 11፥12፤ 52፥11፤ ኤር25፥22፤ 31፥23፤ ሕዝ34፥13
66፥21 ዘፀ19፥6፤ 1ጴጥ2፥5፡9
66፥22 ኢሳ48፥19፤ 65፥17፤ ዮሐ10፥27-29፤ ዕብ12፥26-27፤ 1ጴጥ1፥4-5፤ 2ጴጥ3፥13
66፥23 መዝ22፥29፤ ኢሳ19፥21፤ 44፥5፤ ሕዝ46፥1-3፤ ራእ15፥4
66፥24 መዝ110፥6፤ ኢሳ1፥2፤ 14፥11፤ ማቴ25፥41፤ ማር9፥48

[u]18 በዕብራይስጡ የዚህ ሐረግ ትርጒም በትክክል አይታወቅም።

66፥13 *በኢየሩሳሌምም ትጽናናላችሁ፤* 49፥13 እና ማብ ይመ፤ ከ2ቆሮ1፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ።

66፥14 *ልባችሁ ሐሤት ያደርጋል፤* 60፥5 ይመ። *ሣር፤* የደካማነት ምልክት መሆኑ ይታወቃል፤ 37፥27 እና ማብ ይመ፤ 51፥12 ይመ፤ ሆኖም ከ44፥4 ጋር ያወዳድሩ። *የእግዚአብሔር እጅ፤* ከዕዝ7፥9፤ 8፥31 ጋር ያነጻጽሩ። *ከባሮቹ፤* 54፥17 እና ማብ ይመ። *ቍጣው፤* ቍ15፤ 13፥13 እና ማብ ይመ።

66፥15-16 *በእሳት፤* ፍርድ የሚገለጥበት ቃል ነው (1፥13 እና ማብ 30፥27 ይመ)።

66፥15 *ሠረገላዎቹም እንደ ዐውሎ ነፋስ፤* 5፥28፤ 2ነገ2፥11፤ 6፥17፤ መዝ68፥17 ይመ። *በቍጣ፤* 34፥2፤ 42፥25 እና ማብ ይመ። *ተግሣጹንም፤* 51፥20 እና ማብ ይመ።

66፥16 *በሰይፍ፤* 27፥1፤ 34፥6 እና ማብ ይመ። *ፍርዱን ... ያመጣል፤* በጌታ ቀን ማለት ነው (የ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ ከሕዝ 38፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ)።

66፥17 *አትክልት ቦታዎች፤* 1፥29 እና ማብ ይመ። *ራሳቸውን የሚቀድሱና የሚያነጹ፤* የአምልኮ ጣዖት ሥርዐት በሚጠይቃቸው መንገድ ሁሉ ማለት ነው፤ ከ2ዜና30፥17 ጋር ያነጻጽሩ። *የዕሪያዎችንና ... ሥጋ፤* 65፥4 እና ማብ ይመ።

66፥18 *ሐሳባቸውን፤* 65፥2 እና ማብ ይመ። ለዚህ ነገር በቅድሚያ ተጠያቂዎቹ ከሓዎቹ እስራኤላውያን ናቸው። *መንግሥታትንና ... ሁሉ ልሰበስብ፤* ከኢል3፥2፤ ሶፎ3፥8፤ ዘካ14፥2 ጋር ያነጻጽሩ። *ክብሬንም ያያሉ፤* እግዚአብሔር ሕዝቡን ከሚታደግበት ሁኔታ ጋር የተያያዘ ነው (35፥2-4፤ 40፥5 እና ማብ ይመ)።

66፥19 *ምልክት፤* ምናልባት በ11፥10፡12 የተጠቀሰውን ዐርማ ሊሆን ይችላል (የ5፥26 ማብ ይመ፤ ከመዝ74፥4 ጋር ያነጻጽሩ)። በዳግም ምጽአት ከተጠቀሰው፣ "ከሰው ልጅ ምልክት" ጋር ይህን ያነጻጽሩ (ማቴ24፥30)። *የተረፉትን፤* ከፍርድ በኋላ ማለት ነው (ቍ16 ይመ)፤ ከዘካ14፥16 ጋር ያነጻጽሩ። *ተርሴስ፤* 23፥6 እና ማብ ይመ። *ፉጥ፤* ከግብፅ በስተ ምዕራብ ዛሬ ሊቢያ በሚባለው አገርና በአካባቢው የሚኖሩ ሰዎች ናቸው፤ ናሆ3፥9 ይመ። *ሉድ፤* በምዕራቡ ማዕከላዊ ትንሹ እስያ ያሉትን (በዘፍ10፥13 እና ማብ ይመ) ወይም በአፍሪካ ያሉትን ሕዝቦች ሊያመለክት ይችላል። *ቀስተኞች፤* ኤር46፥9 ይመ። *ቶባል፤* ብዙውን ጊዜ ከሜሴቅ ጋር አብሮ የሚጠቀስ ስም ነው (ዘፍ10፥2 እና ማብ፤ ሕዝ27፥13፤ 38፥2-3፤ 39፥1 ይመ)። ይህም ስፍራ ምናልባት ከጥቁር ባሕር በስተ ደቡብ ምሥራቅ ሳይሆን አይቀርም። *ደሴቶች፤* 11፥11 እና ማብ ይመ። *ክብሬን ይናገራሉ፤* 42፥12፤ 1ዜና16፥24 ይመ።

66፥20 *ወንድሞቻችሁን ሁሉ ... ያመጧቸዋል፤* አሕዛብ የተረፉትን ሰብስበው ያመጣሉ ማለት ነው (11፥11-12፤ 49፥22፤ 60፥4 እና ማብ ይመ)። *ወደ ተቀደሰው ተራራዬ፤* 2፥2-4 እና ማብ ይመ። *ቍርባናቸውን ... ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፤* እስራኤላውያን ዐሥራታቸውንና መባቸውን እንደሚያመጡ (ዘዳ12፥5-7 ይመ)።

66፥21 *አንዳንዶቹን፤* ያመኑትን አይሁድ (61፥6 እና ማብ) ወይም ወደ ቤተ ክርስቲያን የተጨመሩትንና የመሲሑ መንግሥት ዜጎች (1ጴጥ2፥5፡9 እና ማብ ይመ) የሆኑትን አሕዛብ ያመለክታል።

66፥22 *አዲስ ሰማያትና አዲስ ምድር፤* 65፥17 እና ማብ ይመ። *የዘራችሁ ስም እንደዚሁ ጸንቶ ይኖራል፤* 48፥19 እና ማብ ይመ።

66፥23 *ከአንዱ ወር መባቻ፤* 1፥14 እና ማብ ይመ። *የሰው ልጅ ሁሉ ... ሊሰግድ፤* 19፥21፤ ዘካ14፥16 እና ማብ ይመ።

*66፥24፤* በማር9፥48 ላይ በከፊል ተጠቅሶአል። *ወጥተውም ... ያያሉ፤* የሂኖም ሸለቆ ከኢየሩሳሌም በስተ ደቡብ ምዕራብ የሚገኝ ሲሆን፣ የገሃነም ምሳሌ ነው፤ ነህ11፥30፤ ኤር7፥32 ይመ። *ሬሳ፤* 5፥25፤ 34፥3 ይመ። *ያመፁትን፤* 1፥2 እና ማብ 24፥20 ይመ። *ትላቸው አይሞትም፤* ዘላለም ሲቃጠሉ መኖርን ያመለክታል፤ 14፥11፤ 48፥22፤ 50፥11፤ 57፥21 ይመ። *እሳታቸው አይጠፋም፤* 1፥31 እና ማብ፤ ማቴ3፥12 ይመ። *አስጸያፊ፤* ዳን12፥2 ይመ።

# ትንቢተ ኤርምያስ

## *መግቢያ*

### *ጸሐፊው፣ መጽሐፉ የተጻፈበት ጊዜ*

ይህ መጽሐፍ ከሌሎች የብሉይ ኪዳን ነቢያት መጻሕፍት ይልቅ የነቢዩ ኤርምያስን የግል ሕይ ወት መከራና አገልግሎቱ ምን እንደሚመስል የሚገልጽ መጽሐፍ ነው:: የስሙ ትርጉም በግልጽ አይ ታወቅም፤ ነገር ግን አንዳንድ ሐሳቦች ተሰጥተዋል:: "እግዚአብሔር ከፍ ያደርጋል"፣ "እግዚአብሔር ይመሠርታል" የሚሉት ከተሰጡት ትርጉሞች መካከል ጥቂቶቹ ሲሆኑ፣ በይበልጥ ተቀባይነት ያለው ግን፣ "እግዚአብሔር ይወረውራል" የሚለው ነው ወይም በኀጢአታቸው ምክንያት ከእግዚአብሔር ፍርድ ሥር፣ የአሕዛብን "ወደ ታች መወርወር" ሊያመለክት ይችላል:: ኤርምያስ የነቢይነት አገልግሎቱን የጀመረው በ626 ዓ.ቅ.ክ. ሲሆን፣ የፈጸመውም በ586 ዓ.ቅ.ክ በኋላ ነው (የ1፥2-3 ማብ ይመ)::

የሶፎንያስ አገልግሎት ከኤርምያስ አገልግሎት ጥቂት ቀደም የሚል ሲሆን፣ ዕንባቆምና ምና ልባትም አብድዩ ያገለግሉ የነበረው ከኤርምያስ ጋር በተመሳሳይ ጊዜ ነበር:: ነቢዩ ሕዝቅኤል አገል ግሎቱን በ593 ዓ.ቅ.ክ በባቢሎን ቢጀምርም፣ የመጨረሻው የአገልግሎት ዘመኑ በኢየሩሳሌም የነበረው ታላቁ ነቢይ ኤርምያስ ያገለግል ከነበረበት ጊዜ ጋር አንድ ነው:: ነቢዩ ኤርምያስ እንዴትና መቼ እንደ ሞተ በትክክል የሚታወቅ ነገር የለም፤ ይሁን እንጂ በግብፅ ተሰዶ ሳለ በድንጋይ ተወግሮ እንደ ሞተ የአይሁድ ትውፊት ይናገራል (ከዕብ 11፥37 ጋር ያነጻጽሩ)::

ኤርምያስ ካህንና የኬልቅያስ ቤተ ሰው ወገን ነበር፤ የትውልድ አገሩ አናቶት ሲሆን (1፥1)፣ በንጉሥ ሰሎሞን ጊዜ ካህን የነበረው የአብያታር ወገን ሳይሆን አይቀርም (1ነገ2፥26):: በይሁዳ ያለው ቀጣይ ትውልድ በእግዚአብሔር መለኮታዊ ፍርድ ተጠራርጎ የሚጠፋበት ጊዜ ሩቅ ስላልነበረ፣ እግዚ አብሔር ኤርምያስን ሚስት እንዳያገባና ልጆችን ወልዶ እንዳያሳድግ አዘዘው (16፥1-4):: ኤርምያስ ገና ከመጀመሪያው የሚናገረው የትንቢት ቃል ፍርድንና ጥፋትን ያዘለ ነበር፤ ያፈራቸውም ወዳጆች እጅግ ጥቂት ሲሆኑ፣ ከእነርሱም መካከል አኪቃም (26፥24)፣ የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስና (39፥14) ኢትዮጵ ያዊው አቤሜሌክ (38፥7-13፤ ከ39፥15-18 ጋር ያነጻጽሩ) ይገኙበታል:: የኤርምያስ የቅርብ ጓደኛና ታማኝ ጸሐ ፊው የነበረው ባሮክ ሲሆን፣ እርሱም ነቢዩ ኤርምያስ በቃሉ የተናገረውን የእግዚአብሔር ቃል በቀጥታ ይጽፍ ነበር(36፥4-32):: ባሮክ ምድራዊን ነገር ለማግኘት ያለውን ምኞት ገትቶ፣ እግዚአብሔር ዕድል ፈንታ አድርጎ በሰጠው ነገር ብቻ እንዲረካ ነቢዩ ኤርምያስ መክሮታል (ም 45):: ባሮክ የግዢ ውል የተፈጸመበትን ሠነድ ከኤርምያስ ተቀብሎ በሸክላ ዕቃ ውስጥ በጥንቃቄ እንዲቀመጥ አደረገ (32፥11-16)፤ በኋላም ነቢዩ ተሰዶ ወደ ሄደበት ወደ ግብፅ አብሮት በመሰደድ ረጅም መንገድ ከእርሱ ጋር ተጓዘ (43፥6-7):: ከም 1-51 ከተጠቀሱት ድርጊቶች ውስጥ በ580 ዓ.ቅ.ክ በኋላ የተፈጸመ ነገር ስለ ሌለ፣ የነቢዩ ኤርምያስን መጽሐፍ አጠቃሎ የጻፈውና ያዘጋጀው ያለ ጥርጥር ራሱ ባሮክ ነው (ም 52 በሌላ ሰው እጅ ተጽፎ የገባ ተጨማሪ ታሪክ ነው)::

ኤርምያስ ለምርመራና ለግል ሂስ ራሱን ግልጥ በማድረጉ ባሕርዩና ማንነቱ ምን እንደ ሚመስል በሚገባ አሳይቶአል (10፥24):: በተፈጥሮው ፈሪ ቢሆንም (1፥6)፣ እግዚአብሔር ብርቱና ደፋር እንደ ሚያደርገው አረጋግጦለታል (1፥18፤ 6፥27፤ 15፥20):: በተናገራቸው የንስሐ ቃሎች ውስጥ (11፥18-23፤ 12፥1-4፤ 15፥10-21፤ 17፥12-18፤ 18፥18-23፤ 20፥7-18)ግልጽ በሆነ ሁኔታ ስሜቱን ለእግዚአብሔር በመንገር፣ ጥልቅ የሆነውን ውስጣዊ ትግል ገልጦአል (12፥1:15፥18):: ለወገኖቹም እጅግ የማለደ ቢሆ ንም አንዳንድ ጊዜ ደግሞ በግል ጠላቶቹ ላይ በቀልን የሚጋብዝ የርግማንና የውግዘት ቃልን ተጠ ቅሞአል (12፥1-3፤ 15፥15፤ 17፥18፤ 18፥19-23):: ኤርምያስ አብዛኛውን ጊዜ መንፈሱ በሐዘን የተሰበረ ስለ ነበር (4፥19፤ 9፥1፤ 10፥19-20፤ 23፥9)፣ "አልቃሻው ነቢይ" በመባል ይታወቃል:: ይሁን እንጂ ከእግዚአብሔር የተቀበለውን መለኮታዊ ጥሪ በማሰቡና (1፥17) እግዚአብሔርም በተደጋጋሚ ነቢይ አድርጎ እንደ ላከው ስላረጋገጠለት (3፥12፤ 7፥2: 27-28፤ 11፥26፤ 13፥12-13፤ 17፥19-20) በእግዚአ ብሔር አገልግሎት ውስጥ ፈሪ እንዳይሆን አድርጎታል (ከ15፥20 ጋር ያነጻጽሩ)::

### *ታሪካዊ ዳራ*

ነቢዩ ኤርምያስ በይሁዳ ትንቢት የተናገረው ከኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት (ዓ.ቅ.ክ 640-609) አጋማሽ ጀምሮ እስከ ኢዮአካዝ (ዓ.ቅ.ክ 609)፣ ኢዮአቄም (ዓ.ቅ.ክ 609-598)፣ ዮአኪን (ዓ.ቅ.ክ 598-597) እና ሴዴቅያስ (ዓ.ቅ.ክ 597-586)ዘመነ መንግሥት ድረስ (ከዚያም በኋላ) ነው:: ይህ ጊዜ ይሁዳን ጨምሮ አያሌ መንግሥታትና ሕዝቦች ብዙ መከራ ያዩበት የሥቃይና የጭንቀት ዘመን ነበር:: በምዕራብ እስያ የሚገኙ ትናንሽ መንግሥታት፣ ግዛታቸውን ለማስፋፋት በሚታገሉና በሚፎካከሩ እንደ ግብፅ፣ አሦርና ባቢሎን ባሉ መንግሥታት ይደቈሱና ይረገጡ ነበር፤ ኤርምያስ ያገለግልበት የነበረበት ዘመን ገጽታ ከዚህ የተለየ አልነበረም:: አሹርባኒፓል ከአሦር ታላላቅ ነገሥታት አንዱና የመጨረሻው ንጉሥ ሲሆን፣ የሞተውም በ627 ዓ.ቅ.ክ ነው:: ከተተኪዎቹም መካከል አገዛዙን በ626 ዓ.ቅ.ክ እንደ ጀመረውና አዲሲቷን የባቢሎንን መንግሥት እንደ መሠረተው እንደ ናቡፖላሳር ያለ አልነበረም:: ኤርምያስም ለነቢይነት አገልግሎት የተጠራው በዚሁ ዓመት ነበር:: የአሦር መዲና የነበረችው ነነዌ በ612 ዓ.ቅ.ክ

በባቢሎናውያንና በሜዶናውያን የተባበረ ሰራዊት ጥቃት ሥር ከወደቀች በኋላ፣ ከባቢሎን ጋር ወዳጅነት ያልነበራት ግብፅ ልትወድቅ የተቃረበችውን አሦርን ለማዳን ወደ ሰሜን ዘመተች። የይሁዳ ንጉሥ ኢዮስያስ የግብፅን ግሥጋሴ ለመግታት ያደረገው ሙከራ ትልቅ ስህተት ስለ ነበረ፣ በ609 ዓ.ቅ.ክ በፈርዖን ኒካው ዳግማዊ በመጊዶ አቅራቢያ አሳዛኝ በሆነ ሁኔታ ያለ ጊዜው ተገደለ (2ዜና35፥20-24)። ነቢዩ ኤርምያስ እንደ እርሱ እግዚአብሔርን ይፈራ የነበረው ኢዮስያስ መንፈሳዊ ተሃድሶን በአገሪቱ ባደረገ ጊዜ በ11፥1-8፤ 17፥19-27 ላይ የተጠቀሱትን መልእክቶች የተናገረው ራሱ ሊሆን ይችላል፤ ይህ ንጉሥ አሳዛኝ በሆነ ሁኔታ ያለ ጊዜው ሲሞትም የሐዘን ግጥም ገጠመለት (2ዜና35፥25)።

ሰሎም በመባል የሚታወቀው የኢዮስያስ ልጅ ኢዮአካዝ፣ ጥሩ ስላልነበረው አካሄዱ በኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ አጭር መግለጫ ተሰጥቷል (22፥10-12) ፈርዖን ኒካው ኢዮአካዝን በሰንሰለት በማሰር፣ ኤልያቄም የተባለውን የኢዮስያስን ልጅ ኢዮአቄም የሚል ስም አውጥቶለት በምትኩ አነገሠው። ኢዮአካዝ ለአጭር ጊዜ ማለትም ለሦስት ወር ያህል ገዛ (2ዜና36፥2)፤ የእርሱም የአገዛዝ ዘመን ቤተ መንግሥቱ በኤርምያስ ላይ በነበረው አመለካከት ላይ ትልቅ ለውጥ አምጥቶአል። ቀደም ብሎ ኤርምያስ የንጉሡ ወዳጅና የግል ምስጢረኛ ነበር፤ አሁን ግን ለአጭር ጊዜ በነጻነት ከኖረ በኋላ የእስር ና የስደት ኑሮ ተፈራረቀበት (20፥1-2፤ 26፥8-9፤32፥2-3፤ 33፥1፤ 36፥26፤37፥12-21፤ 38፥6-13:28)።

ኢዮአቄም ለኤርምያስ ባለው ጠላትነት ገፋበት። አንድ ጊዜ የነቢዩ ኤርምያስ የትንቢት ቃል ሲነበብለት (36፥21)፣ ንጉሡ የጸሐፊ ቢላዋ በመያዝ ሦስት ወይም አራት ዐምድ በተነበበለት ቍጥር እየቀደደ በክረምት ቤቱ ውስጥ ባለው የእሳት ምድጃ ላይ ይጥለው ነበር (ቍ22-23)። ይሁን እንጂ ኤርምያስ በእግዚአብሔር ትእዛዝ ብዙ ተመሳሳይ ቃላትን በመጨመር ለባሮክ ተናግሮ የትንቢቱ ቃል ለሁለተኛ ጊዜ እንዲጻፍ አደረገ (ቍ32)።

በኤርምያስ ሕይወት ላይ ከተከሠተው ከዚህ ሁኔታ በፊት፣ የታሪክን ሂደት የለወጠ አንድ ለየት ያለ ነገር ተፈጽሞአል። በ605 ዓ.ቅ.ክ በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ ከርከሚሽ ላይ ግብፆች አባቱን ናቡፖላሳርን በዚያው ዓመት ተክቶ የባቢሎን ገዥ በሆነውና ልዩ ችሎታ በነበረው ጦር መሪ በናቡከደነፆር ተደመሰሱ (46፥2)። ፈርዖን ኒካው ከፍተኛ ሽንፈት ደርሶበት ወደ ግብፅ ተመለሰ፤ ባቢሎንም ለሚቀጥሉት 70 ዓመታት በምዕራባዊ እስያ ያለ ተፎካካሪ የበላይ ሆና ቈየች። ስለዚህ ናቡከደነፆር በ605 ዓ.ቅ.ክ ኢየሩሳሌምን ከበበ፤ ኢዮአቄምን ከዙፋኑ አወረደ (ዳን1፥1-2)፤ ዳንኤልንና ሌሎች ሦስት ጓደኞቹን ወደ ባቢሎን አፈለሰ (ዳን1፥3-6)። ከዚህ በኋላበ 598-597 ዓ.ቅ.ክ ናቡከደነፆር እንደ ገና ኢየሩሳሌምን ወጋ፤ ከዚህ በኋላ ስለ ዐመፀኛው ኢዮአቄም ምንም ወሬ አልተሰማም። ልጁ ዮአኪን ለሦስት ወር ብቻ ይሁዳን ገዛ (2ዜና36፥9)። ነቢዩ ኤርምያስ የዮአኪንንና የተከታዮቹን ተማርኮ መሄድ አስቀድሞ የተናገረ ሲሆን (22፥24-30)፣ ይህም ትንቢት ቈይቶ ተፈጽሞአል (24፥1፤ 29፥1-2)።

በ597 ዓ.ቅ.ክ ዓመት የኢዮስያስ ልጅ የሆነውን የዮአኪንን አጎት ማታንያንን፣ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ስሙን ሴዴቅያስ ብሎ በይሁዳ አነገሠው (37፥1፤ 2ነገ24፥17፤ 2ዜና36፥11-14)። ሴዴቅያስ ደካማና ወላዋይ ንጉሥ ነበር። አንዳንድ ጊዜ የነቢዩ ኤርምያስ ወዳጅ በመሆን ምክር ሲጠይቀው፣ በሌላ ጊዜ ደግሞ የነቢዩን ጠላቶች ወሬ በመስማት ኤርምያስን ያጕሳቍለውና ያስረው ነበር። የሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት ሊያበቃ በተቃረበበት ጊዜ፣ ነቢዩ ኤርምያስ የራሱን ሕይወት ለማትረፍ ሲል፣ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ሊገልጽለት ከንጉሡ ጋር ተስማማ (38፥15-27)። ከዚህ ጊዜ በኋላም ቢሆን ኢየሩሳሌም ሙሉ በሙሉ እስከ ተያዘችበት እስከ በ586 ዓ.ቅ.ክ (38፥28) ድረስ የቁም እስረኛ ሆኖ ቈይቶአል።

ሴዴቅያስ ከከተማይቱ ሸሽቶ ለማምለጥ ሲሞክር፣ ባቢሎናውያን ተከታትለው ያዙት፤ ልጆቹንም በፊቱ ገደሏቸው፤ ከዚህም በኋላ ናቡከደነፆር የሴዴቅያስን ዐይን አወጣ (39፥1-7)። የንጉሡ ዘበኞች አለቃ የነበረው ናቡዘረዳን፣ ናቡከደነፆር የይሁዳ ገዥ አድርጎ ከሾመው ከጎዶልያስ ጋር እንዲቀመጥ ኤርምያስን መከረው (40፥1-6)። ጎዶልያስ ይሁዳን ጥቂት ጊዜ እንደ ገዛ በተቃዋሚዎቹ ተገደለ (ም41)። ሌሎቹ አይሁዶች የባቢሎናውያንን የበቀል ጥቃት በመፍራት፣ ኤርምያስንና ባሮክን ይዘው ወደ ግብፅ ሸሹ (43፥4-7)። በዚህ ጊዜ የነቢዩ ኤርምያስ ዕድሜ ከ70 በላይ ሳይሆን አይቀርም። በትንቢቱ የተጻፈው የመጨረሻ ቃል በ44፥24-30 ላይ የሚገኝ ሲሆን፣ በዚህ ክፍል ያለው የመጨረሻ ቃልም ግብፅን በ589-570 ዓ.ቅ.ክ ስለ ገዛው ስለ ፈርዖን ሖፍራ የተጻፈ ብቸኛ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ ነው።

## መልእክቱና በውስጡ የተካተቱ ዋና ሐሳቦች

በስሙ በሚታወቀው መጽሐፍ ውስጥ በተደጋጋሚ፣ "ነቢዩ ኤርምያስ" ተብሎ (20፥2፤ 25፥2፤ 28፥5:10-12:15፤ 29፥1:29፤ 32፥2፤ 34፥6፤ 36፥8:26፤ 37፥2:3:6፤ 38፥9-10:14፤ 42፥2:4፤ 43፥6፤ 45፥1፤ 46፥1:13፤ 47፥1፤ 49፥34፤ 50፥1) እንዲሁም በሌላ ስፍራ በተመሳሳይ ሁኔታ የሚጠራው (2ዜና36፥12፤ ዳን9፥2፤ ማቴ2፥17፤ 27፥9፤ ማቴ16፥14 ይመ) ኤርምያስ ለነቢይነት አገልግሎት በእግዚአብሔር መጠራቱን ምንጊዜም ቢሆን የሚዘነጋው አልነበረም (1፥5፤ 15፥19)። ስለሆነም ኤርምያስ በራሱ በእግዚአብሔር አስቀድሞ የተነገረውን የትንቢት ቃል ብቻ ተናገረ (19፥2)፤ የተናገረውም ሙሉ በሙሉ ተፈጸመ (28፥9፤ 32፥24)። / ኤርምያስ እንደ ሐናንያ (ም;28) ሸማያ (29፥24ጠ32) ያሉ ሐሰተኛ ነቢያትን አጥብቆ የሚቃወምና ፊት የማይሰጥ ሰው ነበር (14፥13-18፤ 23፥13-40፤ 27፥14-18)። እርሱ የተናገራቸው አብዛኛዎቹ ትንቢቶች በአጭር ጊዜ የተፈጸሙ ሲሆን (16፥15፤ 20፥4፤ 25፥11-14፤ 27፥19-22፤

29፥10፤ 34፥4-5፤ 43፥10-11፤ 44፥30፤ 46፥13)፤ ሌሎቹ ደግሞ በረጅም ጊዜ ውስጥ የተፈጸሙ ወይም ወደ ፊት ሊፈጸሙ ያሉ ነበሩ (23፥5-6፤ 30፥8-9፤ 31፥31-34፤ 33፥15-16)::

አስቀድሞ እንደ ተገለጸው የኤርምያስ አገልግሎት ገና ከመጀመሪያው በግጭት የተሞላ ነበር:: ልጆቻቸውን ለባዕድ አማልክት እንዲሠዉ የሚያስገድዳቸውን ጣዖት በማምለክ ስላመነዘሩ (16፥10-13:20፤ 22፥9፤ 32፥29፤ 44፥2-3:8:17-19:25)፣ የአገሩን ሰዎች በሠሩት ኀጢአት ክፉኛ ወቅሶአቸዋል (44፥23):: ነገር ግን የይሁዳ ሰዎች ኀጢአት ቢሠሩ እንኳ ኤርምያስ ይወዳቸዋል፤ እግዚአብሔር ባይፈቅድለትም (7፥16፤ 11፥14፤ 14፥11) ስለ እነርሱ ከመጸለይ ወደ ኋላ አላለም (14፥7:20)::

ንስሐ እውነተኛ ከሆነ፣ ፈጥኖ ሊፈጸም ያለውን ቅጣት ሊያግድ እንደሚችል ኤርምያስ በጥንቃቄ ቢያመለክትም፣ ፍርድ በሁሉ ስፍራ ግልጽ ሆነው ከሚገኙት የመጽሐፉ ዋና ሐሳቦች አንዱ ነው:: እስራ ኤላውያን ለባቢሎናውያን እንዲገዙና ቀደም ብለው ተማርከው የሄዱትም ባሉበት ቦታ ሕይወታቸውን በቀድሞው ሁኔታ እንዲመሩ የሰጠው ምክር ኤርምያስን በብዙዎች ዘንድ እንደ ከዷ አስቈጥሮታል:: በሌላ በኩል ደግሞ የአገሩ ሰዎች እንዳያምፁ መምከሩና ራሳቸውን ሲያጠፉ ዝም ብሎ አለመመ ልከቱ፣ ሕዝቡን የሚወድ እውነተኛ ዐርበኛ አድርጎታል:: በባቢሎን ላይ ከማመፅ ይልቅ መገዛት እንዳለባቸው በማስጠንቀቅ፣ ኤርምያስ በማንኛውም ሁኔታ ቢሆን ሊጠበቅ የሚገባውን፣ ለእነርሱ የሆነውን የእግዚአብሔርን ፈቃድ ገልጦላቸዋል::

ነቢዩ ኤርምያስ እግዚአብሔር የሁሉ ነገር የበላይ መሆኑን በሚገባ ተረድቶአል:: በኤርምያስ የትምህርተ መለኮት አስተምህሮ መሠረት እግዚአብሔር የተፈጠሩ ነገሮች ሁሉ ፈጣሪ (10፥12-16፤ 51፥15-19)፣ ሁሉን ቻይ (32፥27፤ 48፥15፤ 51፥57)፣ በሁሉ ስፍራ የሚገኝና ሁሉንም የሚያውቅ (23፥24) ነው:: ኤርምያስ የሚያገለግለውን አምላክ እጅግ ከፍ ከፍ በማድረግ (32፥17-25)፣ የይሁዳ ብቻ ሳይሆን፣ የአሕዛብና የመንግሥቶቻቸው ጌታና ገዥ እንደ ሆነ ገልጾአል (5፥15፤ 18፥7-10፤ 25፥17-28፤ ምዕራፍ 46-51)::

በተጨማሪም ኤርምያስ፣ እግዚአብሔር ስለ ግለሰቦችና በእርሱም ዘንድ ስላላቸው ኀላፊነትና ተጠ ያቂነት ግድ የሚለውና የሚጠነቀቅ ሰው ነው:: ነቢዩ ኤርምያስ በዚህ ነገር ላይ ያደረገው ትኵረት (31፥29-30)፣ ነቢዩ ሕዝቅኤል ካደረገው ጋር እጅግ ተመሳሳይ ነው (ሕዝ18፥2-4)፤ ስለዚህም ሁለቱ ነቢ ያት፣ "ስለ ሰዎች የሚጨነቁ ነቢያት" በሚል ይታወቁ ነበር:: የሚወዳት ይሁዳ ወደ ሞት እየተነዳች ሲመለከት፣ ኀጢአትንና የውጤቱን አይቀሬነት ተገንዝቦ ከእግዚአብሔር የተሰጠውን ኀላፊነት ለመወ ጣት ነቢዩ ኤርምያስ ኀይለኛ የጽድቅ ሰባኪ ሆነ (5፥14፤ 20፥9፤ 23፥29)፤ ዘመናት ቢያልፉም ኤርምያስ የተናገረው የትንቢት ቃል ግን ኀይሉን አላጣም::

ኢዮስያስ ለአጭር ጊዜ ያህል መንፈሳዊ ተሐድሶን በይሁዳ ቢያደርግም፣ በረጅሙና በክፉው የምናሴ ዘመነ መንግሥት ምድሪቱ እጅግ በኀጢአት ተበክላ ነበር:: ለእንዲህ ዐይነቷ ምድር የእግዚ አብሔርን ፍርድ ማወጅ፣ ደስ ለማያሰኝ አገልግሎት መጠራት ነው:: ይሁን እንጂ እግዚአብሔር በራ ሱ ሕዝብ ላይ ፍርድ እንደሚያመጣ መናገር፣ እንዲሁም የዘመኑ ፍጻሜ መቃረቡን ማወጅ ነበረበት:: ከረጅም ጊዜ በኋላ እግዚአብሔር የመጨረሻውን የቃል ኪዳኑን ርግማን (ዘሌ26፥31-33፤ ዘዳ28፥49-68) በቀረው ሕዝቡ ላይ ማምጣት ነበረበት:: ከግብፅ ካወጣቸው ቀን ጀምሮ ያደረገላቸውን ነገር ሁሉ ያጠ ፉል:: ይህም እስራኤላውያን እልከኛ በመሆን፣ ልባቸውን ባለመቀደስና በመዘጋት መቃጠላቸው፣ ዕጣ ፈንታቸውም ምን እንደሆነ የሚገልጽ የመጨረሻው ቀን የተቃረበ የሚመስልበት ጊዜ ነው:: በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር የመረጠው ሕዝብ መጣሉን፣ የጥንት ተስፋዎችና ቃል ኪዳኖች ሁሉ ከንቱ ሆነው መቅረ ታቸውን መገንዘብ ይቻላል::

እግዚአብሔር በሕዝቡ ላይና በአሕዛብ መንግሥታት ላይ የሚያመጣው ፍርድ አስፈሪ ቢሆንም፣ ይህ ታዲያ እግዚአብሔር በታሪክ ውስጥ የሚሠራው የመጨረሻው ነገር አልነበረም:: ምሕረትና የኪዳን ታማኝነት ቍጣን አሸንፈው ይወጣሉ:: ከፍርድ በኋላ እንደ ገና መቋቋምና መታደስ ይመጣል:: እስራ ኤል እንደ ገና ትቋቋማለች፤ ያፈራረሷት መንግሥታት ይፈርሳሉ፤ እግዚአብሔር ከእስራኤል፣ ከዳዊትና ከሌዋውያን ጋር የገባው የጥንቱ ኪዳን ይከበራል:: እግዚአብሔር እንደ ገና ከሕዝቡ ጋር አዲስ ኪዳን ያደር ጋል፤ ሕጉን በሕዝቡ ላይ ይጽፋል:: (31፥31-34) ለአገልግሎቱም ይቀድሳቸዋል:: የዳዊት ቤት በጽድቅ ይገዛቸዋል፤ ታማኝ ካህናትም ያገለግላሉ:: እግዚአብሔር ለእስራኤል የሚገባው የቤዛነት ተስፋ፣ በፍጥ ረት ውስጥ እንዳለው ሕግ የጸና ነው (ም:33)::

የኤርምያስ መልእክት የሩቁንም ሆነ የቅርቡን እይታ ግልጽ አድርጎታል:: ለእስራኤል አምላክ ታማኝ ባልሆነችው እስራኤል ላይ በማስመሰል፣ ሐሰተኛ ነቢያት ለዐመፀኛው ሕዝብ ሰላም እንደሚመጣ ያውጁ ነበር:: ነገር ግን ኀጢአትን እንዲያወግዝና ፍርድን እንዲያውጅ ኤርምያስን ያስገደደው እግዚአብሔር፣ መለኮታዊ ፍርዱ ለ70 ዓመት ያህል እንደ ሚጸና ይናገር ዘንድ ሥልጣን የሰጠው እርሱ ነው:: ከዚህ በኋላ ይቅርታና መንጻት ይመጣል፤ በእግዚአብሔር የጥንት ሥራ፣ ተስፋና ቃል ኪዳን የተጠቀሱ፣ ባለፈው የሚናፈቁ ነገሮች ሁሉ ጥንት እግዚአብሔር ከፈጸማቸው የምሕረት ሥራዎች ሁሉ በላይ በሆነ ሁኔታ የሚፈጸሙበት አዲስ ዘመን ነው::

### ሥነ ጽሑፋዊ ይዘት

ትንቢተ ኤርምያስ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ካሉት መጻሕፍት ይልቅ አያሌ ቃላትን የያዘ ዳጐስ ያለ መጽሐፍ ነው:: በተጨማሪነት የገባውን ታሪካዊ ጽሑፍ (ም52) አካትቶ ብዙ ምዕራፎች በስድ ንባብ

ቢጻፉም (ም7፤ 11፤ 16፤ 19፤ 21፤ 24-29፤ 32-45)፣ ብዙዎቹ የጽሑፉ ክፍሎች ግጥማዊ ይዘት ያላቸው ናቸው:: የኤርምያስ ቅኔ የከበረ ሐሳብ ያለበት፣ ለስለስ ላለ ሙዚቃ የሚመቹ አጫጭር ግጥሞችን በመያዝ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ከታወቁት ክፍሎች አንዱ ነው:: ኤርምያስ ከተናገራቸው ውብ የሆኑ ሐረጎች በተጨማሪ በቀላሉ ሊታወሱ የሚችሉ አያሌ ምንባቦችም በመጽሐፉ ውስጥ ተካተዋል (2፥13:26-28፤ 7፥4:11:34፤ 8፥20:22፤ 9፥23-24፤ 10፥6-7:10:12-13፤ 13፥23፤ 15፥20፤ 17፥5-9፤ 20፥13፤ 29፥13፤ 30፥7:22፤ 31፥3:15:29-30:31-34፤ 33፥3፤ 51፥10)::

በዚህ መጽሐፍ ውስጥ በልዩ ጥበብ የቀረበ የቅኔ ድግግሞሽ ይታያል (4፥23-26፤ 51፥20-23):: ዋና ሐሳብ ያዘሉ ሐረጎችን ደጋግሞ ማቅረብ አስፈላጊ እንደ ሆነና ውጤት እንዳለው ኤርምያስ በሚገባ ተረድቶአል:: ለምሳሌ:- "ሰይፍ፣ ራብና ቸነፈር" የሚሉ ቃሎች በተለያዩ ጥቅሶች ውስጥ 15 ጊዜ ተጽፈዋል (14፥12፤ 12፥7:9፤ 24፥10፤ 27፥8:13፤ 29፥17-18፤ 32፥24:36፤ 34፥17፤ 38፥2፤ 42፥17:22፤ 44፥13):: እጅግ አስፈላጊና ተገቢ በሆኑ ቦታዎች ላይ ደግሞ ምስጢራዊ ስሞችን ይጠቀማል (የ25፥26፡ 51፥1:41 ማብ ይመ):: የድምፅ ድግግሞሽና የድምፅ ከፍና ዝቅ ማለት በግጥሞቹ ምት ላይ የሚታይ ሌላው የኤርምያስ መጽሐፍ ሥነ ጽሑፋዊ ይዘት ነው (48፥43፤ 51፥2፤ የኢሳ24፥17 ማብ ይመ)::

ሕዝቅኤል እንዳደረገው ሁሉ፣ ኤርምያስም ብዙ ጊዜ መልእክቱን በግልጽ ማስረዳት እንዲችል ምሳሌ ማቅረብ እንዳለበት ትእዛዝ ይሰጠው ነበር:: ለምሳሌ የተበላሸችና ጥቅም የሌላት መታጠቂያን መታጠቅ (13፥1-11)፣ ሸክላን መስበር (19፥1-12)፣ ቀንበርን በአንገት ላይ ማድረግና (ም27) ትልልቅ ድንጋዮችን መግቢያ ላይ ባለው ወለል ሥር መሸሸግ (43፥8-13):: ኤርምያስ ሚስት እንዳያገባና ልጆች እንዳይወልድ (16፥1-4)፣ የሐዘን መብል ወደሚበላበት ወይም ወደ ግብዣ ቤት እንዳይገባ (16፥5-9፣ በትውልድ አገሩ በዓናቶት የዕርሻ መሬት እንዳይገዛ (32፥6-15) እግዚአብሔር የሰጠው ትእዛዝ ምሳሌያዊ ይዘት ያለው ነው:: እግዚአብሔር መልእክቱን ለኤርምያስ ለመግለጽ የሚታዩ የመረጃ መሣሪያዎችን በመጠቀምም ነግሮታል፤ ለምሳሌ የሸክላ ሠሪው ሸክላ (18፥1-10)፣ ሁለት ቅርጫት በለስ (24)::

***አስተዋፅኦ***

በኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ ያለው የትንቢት ቃል አጻጻፍ በሕዝቅኤል መጽሐፍ እንደሚታየው አጻጻፍ ቅደም ተከተልን የያዘ አይደለም:: ቅደም ተከተሉን የጠበቀ ቢሆን ኖሮ፣ በመጽሐፉ ውስጥ ያሉት ክፍሎች አቀማመጥ ቀጥሎ ባለው ሁኔታ ሊቀርብ ይችል ነበር (1፥1-7፥15፤ ም26፤ 7፥16-20፥18፤ ም25፤ ም46-51፤ 36፥1-8፤ ም45፤ 36፥9-32፤ ም35፤ ም21-24፤ ም27-31፤ 34፥1-7፤ 37፥1-10፤ 34፥8-22፤ 37፥11-38፥13፤ 39፥15-18፤ ም32-33፤ 38፥14-39፥14፤ 52፥1-30፤ ም40-44፤ 52፥31-34:: ከዚህ በታች የሚገኘው አስተዋፅኦ የኤርምያስን መጽሐፍ አሁን ባለበት ሁኔታ የሚተነትን ነው::

1. የነቢዩ ጥሪ (ም1)
2. ለይሁዳ የተነገረ ምክርና ማስጠንቀቂያ (ም2-35)
   - ሀ. የይሁዳ ምንዝርና (ም2-6)
   - ለ. ቤተ መቅደስን በሚመለከት የተነገረ መልእክት (ም7-10)
   - ሐ. ቃል ኪዳኑን መተላለፍና ሤራ (ም11-13)
   - መ. ድርቁን በተመለከተ የተነገሩ መልእክቶች (ም14-15)
   - ሠ. የደረሰው ጥፋትና የማጽናናት ቃል (16፥1-17፥18)
   - ረ. ሰንበትን ስለ መቀደስ የተሰጠ ትእዛዝ (17፥19-27)
   - ሰ. ከሸክላ ሠሪው የሚገኝ ትምህርት (ም18-20)
   - ሸ. በነገሥታት፣ በነቢያትና በሕዝቡ ላይ የተነገረ ፍርድ (ም21-24)
   - ቀ. ወደ ባቢሎን ተማርኮ ስለ መወሰድ አስቀድሞ መነገሩ (ም25-29)
   - በ. እስራኤል እንደ ገና ስለ መቋቋሟ የተገባው ተስፋ (ም 30-33)
   - ተ. ተጨማሪ የታሪክ ጽሑፍ (ም34-35)
3. የነቢዩ ሥቃይና ስደት (ም36-38)
   - ሀ. የኤርምያስ ጥቅልል መጽሐፍ ስለ መቃጠሉ (ም36)
   - ለ. የኤርምያስ መታሰር (ም37-38)
4. የኢየሩሳሌም አወዳደቅና ያስከተለው ውጤት (ም39-45)
   - ሀ. የኢየሩሳሌም አወዳደቅ (ም 39)
   - ለ. የጎዶልያስ አነሣሥና መገደል (40፥1-41፥15)
   - ሐ. ወደ ግብፅ መሸሽ (41፥16-43፥13)
   - መ. በግብፅ ባሉት ላይ የተነገረ ትንቢት (ም44)
   - ሠ. ተጨማሪ የታሪክ ጽሑፍ፤ ለባሮክ የተሰጠው ተስፋ (ም45)
5. በአሕዛብ መንግሥታት ላይ የተነገረ ፍርድ (ም46-51)
   - ሀ. በግብፅ ላይ (ም46)
   - ለ. በፍልስጥኤም ላይ (ም 47)
   - ሐ. በሞዓብ ላይ (ም48)

መ. በአሞን ላይ (49፥1-6)
ሠ. በኤዶም ላይ (49፥7-22)
ረ. በደማስቆ ላይ (49፥23-27)
ሰ. በቄዳርና በሐፃር (በዓረብ) ላይ (49፥28-33)
ሸ. በኤላም ላይ (49፥34-39)
ቀ. በባቢሎን ላይ (መ 50-51)

6. ተጨማሪ ታሪክ (ም52)

**1** የኬልቅያስ ልጅ፣ ኤርምያስ የተናገረው ቃል ይህ ነው፤ አባቱ በብንያም አገር በዓናቶት ከሚገኙት ካህናት አንዱ ነበረ። ²*የእግዚአብሔር ቃል* የይሁዳ ንጉሥ፣ የአሞን ልጅ ኢዮስያስ በነገሠ በዐሥራ ሦስተኛው ዓመት ወደ ኤርምያስ *መጣ*፤ ³ደግሞም በይሁዳ ንጉሥ፣ በኢዮስያስ ልጅ በኢዮአቄም ንግሥ ዘመን፤ እንዲሁም በይሁዳ ንጉሥ፣ በኢዮስያስ ልጅ በሴዴቅያስ ንግሥ ዘመን፤ እስከ ዐሥራ አንደኛው ዓመት መጨረሻ ድረስ የኢየሩሳሌም ሕዝብ ተማርኮ እስከ ሄደበት እስከ አምስተኛው ወር ድረስ ወደ እርሱ ይመጣ ነበር።

## የኤርምያስ መጠራት

⁴*የእግዚአብሔር ቃል* ወደ እኔ *መጣ*፤ እንዲህም አለኝ፤

⁵“በማሕፀን ሳልሠራህ ዐወቅሁህ፤
ከመወለድህ በፊት ለየሁህ፤[*]
ለሕዝቦችም ነቢይ እንድትሆን ሾምሁህ።”

⁶እኔም፣ “ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ እንዴት እንደምናገር አላውቅም፤ ገና ሕፃን ልጅ ነኝና” አልሁ።

⁷*እግዚአብሔር* ግን እንዲህ አለኝ፤ “‘ገና ሕፃን ልጅ ነኝ’ አትበል፤ ወደምልክህ ሁሉ ሄደህ፣ ያዘዝሁን ሁሉ ትናገራለህ፤ ⁸እኔ አድንህ ዘንድ ከአንተ ጋር ነኝና አትፍራቸው” ይላል *እግዚአብሔር*።

⁹*እግዚአብሔርም* እጁን ዘርግቶ አፌን ዳሰሰና እንዲህ አለኝ፤ “እነሆ፤ ቃሌን በአፍህ

1፥1 ኢሱ21፥18
1፥2 2ነገ22፥1፤ሕዝ 1፥3፤ሆሴ1፥1፤ኢል 1፥1
1፥3 2ነገ23፥34፤ 24፥17፤ዕዝ5፥12፤ኤር 52፥15
1፥5 ቍ10፤መዝ 139፥13፡16፤ኢሳ 49፥1፤ኤር25፥15-26 ፤ዮሐ10፥36
1፥6 ዘፀ3፥11፤6፥12 ፤1ነገ3፥7
1፥8 ቍ19፤ዘፍ 15፥1፤26፥3፤ኢሱ1፥5 ፤8፥1፤ኤር15፥20፡21፤ 26፥24፤36፥26፤42፥ 11፤20፥11
1፥9 ዘፀ4፥12፤ኢሳ 6፥7

[*]5 *ወይም መረጥሁህ*

*1፥1-3፤* የኤርምያስ መጠራት ታሪካዊ ዳራና መቼቱ አጠር ብሎ የቀረበ ቢሆንም አስፈላጊ ነጥቦች የያዘ ነው።

1፥1 *የ... ቃል፤* 36፥10 ይመ፤ ከዚህም በተጨማሪ ነህ1፥1፤ መክ1፥1፤ አሞ1፥1 ይመ፤ ከዘዳ1፥1 ጋር ያነጻጽሩ። *ኤርምያስ፤* ስለ ስሙ ትርጒም ደግሞ የመጽሐፉን መግቢያ ይመ። ከነቢዩ ሌላ ዘጠኝ የብሉይ ኪዳን ሰዎች በዚህ ስም ተጠርተውበታል (1ዜና5፥24፤ 12፥4፡10፡13፤ ነህ10፥2፤ 12፥1፡34 ይመ)፤ ከእነዚህም መካከል ሁለቱ ሰዎች ከነቢዩ ኤርምያስ ጋር በአንድ ዘመን የኖሩ ናቸው (ኤር35፥3፤ 52፥1)። ኬልቅያስ፤ የስሙ ትርጒም፣ “እግዚአብሔር ዕድል ፈንታዬ ነው” ማለት ነው፤ መኖሪያ ከተማው ዓናቶት በመሆኑ የካህኑ የአብያታር ወገን ሊሆን ይችላል የሚል ግምት አለ (1ነገ2፥26፤ አብያታር በንጉሥ ሰሎሞን ዘመን የነበረ ካህን ነው። ኬልቅያስ በመባል በብሉይ ኪዳን ዘመን በታወቀው ስም፣ የሚጠሩ ሌሎች ሁለት ሰዎች በኤርምያስ ዘመን ነበሩ (29፥3፤ ዕዝ7፥1 እና ማብ ይመ)። *ካህናት*፤ እንደ ሕዝቅኤልና (ሕዝ1፥3) እንደ ዘካርያስ ሁሉ፣ ኤርምያስም ነቢይና ካህን ነበረ። *በዓናቶት*፤ 11፥21-23፤ 32፥6-9 ይመ። በዕብራይስጥ ቋንቋ ስሙ የከነዓናውያን የጦርነት አምላክ የሆነችውን የዓናትን የብዙ ቍጥር ቅርጽ የያዘ ቃል ነው። ዓናቶት፣ ከጥንት የኢያሱ ዘመን (ኢሱ 21፥18) እንዲሁም ከሰሎሞን ዘመን (1ነገ 2፥26) ጀምራ ከክህነት ተግባር ጋር የተያያዘ ታሪክ ያላት ከተማ ነበረች፤ በኤርምያስ ዘመንም ከአረማውያን ጋር የተያያዘው አመሠራረቷ ሳይረሳ አይቀርም። በአሁኑ ዘመን ከኢየሩሳሌም በስተ ሰሜን ምሥራቅ 5ኪ.ሜ ያህል ርቃ የምትገኘው ዓናቶት ይህን ጥንታዊ ስም ይዛለች፤ ሆኖም የጥንቷ ዓናቶት ከዚችኛዋ ከተማ 800 ሜትር ያህል ወደ ደቡብ ምዕራብ ራቅ ብላ ትገኝ ነበር። *በብንያም*፤ ዓናቶት ከአራቱ የሌዋውያን ከተሞች አንዷ ስትሆን፣ በብንያም ነገድ ርስት ውስጥ ትገኝ ነበር (ኢያ21፥17-18)፤ ከምርኮ ከተመለሱ በኋላም ብንያማውያን እንደ ገና በዚችው ከተማ ውስጥ ሰፈሩ (ነህ 11፥31-32)።

1፥2 *የእግዚአብሔር ቃል ... መጣ*፤ በአንድ የትንቢት መጽሐፍ መግቢያ ላይ ከእግዚአብሔር ዘንድ ስለ መጣ መልእክት ለመግለጽ እጅግ የተለመደ አባባል ነው (ሕዝ1፥3፤ ዮና 1፥1፤ ሐጌ 1፥1፤ ዘካ 1፥1 ይመ፤ ከሆሴ 1፥1፤ ከኢል 1፥1፤ ከሚክ 1፥1፤ ከሶፎ 1፥1 ጋር ያነጻጽሩ)። *ወደ ኤርምያስ*፤ ከቍ4 ጀምሮ ኤርምያስ ስለ ራሱ በአንደኛ መደብ ይናገራል(ለምሳሌ ቍ11፡13፤ 2፥1 ይመ)። *በዐሥራ ሦስተኛው ዓመት*፤ 626ዓ.ቅ.ክ ማለት ነው (25፥3 ተመ)። *ኢዮስያስ*፤ 3፥6፤ 36፥2 ይመ። ደግና እግዚአብሔርን የሚፈራ የይሁዳ አገር የመጨረሻው ንጉሥ ነበር። መንፈሳዊ እንቅስቃሴና ተሐድሶ እንዲመጣ ያደርገው የነበረውን ጥረት ኤርምያስ በደስታ ከመመልከቱም በላይ፣ ይደግፈው ነበር (22፥15-16 ይመ)፤ እንቅስቃሴው የተጀመረውም በቈራጥ መንፈስ በ621 ዓ.ቅ.ክ. ነበር (2ነገ22፥3-23፥25፤ 2ዜና 34፥8-35፥19 ይመ፤ ከ2ዜና 34፥3-7 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥3 *ኢዮአቄም*፤ እያንዳንዳቸው ሦስት ሦስት ወር ብቻ ስለ ገዙ፣ ከእርሱ በፊት የነበረው (ኢዮአስ) እንዲሁም ከእርሱ በኋላ የተነሣው (ኢዮአቄም) ስማቸው አልተጠቀሰም። ከአባቱ ከኢዮስያስ አንጻር ሲታይ ኢዮአቄም ጨካኝ ገዥ ነበረ (2ነገ 23፥36-37፤ 2ዜና36፥5 ይመ)፤ ኤርምያስም ይህንኑ ወዲያው ተረድቶአል (22፥13-15፡17-19፤ 26፥20-23 ይመ)። *ከዐሥራ አንደኛው ዓመት ... አምስተኛው ወር*፤ “አቢብ” በተባለው የአይሁድ ወር (ሐምሌ/ነሐሴ) በ586ዓ.ቅ.ክ ማለት ነው (52፥12 ይመ)። ሴዴቅያስ፤ የይሁዳ አገር የመጨረሻው ንጉሥ ነበር፤ በተግባር ረገድም ክፋቱ ከኢዮአቄም አያንስም ነበር (52፥1-2፤ 2ዜና36፥11-14 ይመ፤ እንዲሁም ኤር24፥8፤ 37፥1-2 ይመ)። *ተማርኮ፤* የይሁዳ ሕዝብ በገፍ መማረክና የኢየሩሳሌምና የንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደስ መፈራረስ በአንድ ጊዜ የተፈጸመ ሲሆን፣ ያፈረሰው ንጉሥ ናቡከደነፆር፣ በ586 ዓ.ቅ.ክ ነበር (2ነገ25፥8-11 ይመ)።

*1፥4-19፤* የኤርምያስን ጥሪ የሚገልጠው ትረካ ሁለት የትንቢት ራእዮችን ያዘለ ነው (ቍ10-16)፤ የምክርና የማበረታቻ ቃላትም አሉበት (ቍ17-19)።

*1፥4፤* የቍ2 ማብ ይመ።

*1፥5፤* መሳ13፥5፤ ገላ1፥15 ይመ። *ሳልሠራህ* ኢሳ49፥5 ይመ። ኤርምያስን ወደ አገልግሎቱ ለማስገባት፣ የእግዚአብሔር የመፍጠር ሥራ (ዘፍ2፥7፤ መዝ119፥73) የሉዓላዊ ሥልጣኑ መሠረት ነው (18፥4-6፤ ኢሳ43፥21 ይመ)። *ዐወቅሁህ፤* ይህ የሚያመለክተው እግዚአብሔር ኤርምያስን በገዛ ፈቃዱ እንደ መረጠው ነው። እዚህ ላይ የገባውም የዕብራይስጡ ግስ በዘፍ 18፥19፤ በአሞ3፥2 ላይ “መምረጥ” በሚለው ትርጒሙ ተቀምጦአል። *ሾምሁህ፤* ለዚህ ቃል የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል ቍ10 ላይ ካለው ጋር አንድ አይደለም፤ ይሁን እንጂ ሁለቱም የነቢዩን ለአገልግሎት መለየትና መሰየም ያመለክታሉ። *ነቢይ*፤ ቃል በቃል ትርጒሙ፣ የእግዚአብሔርን ሐሳብ ለሰው ለመንገር “የተጠራ ሰው” ማለት ነው (ዘፀ7፥1-2፤ 1ሳሙ9፥9 እና ማብ ይመ)። *ሕዝቦች*፤ የይሁዳ አጎራባች አገሮችን በቅድሚያ የሚያመለክት ቢመስልም (25፥8-38፤ ምዕ46-51)፣ ይሁዳን አይጨምርም ማለት አይቻልም።

1፥6 *እንዴት እንደምናገር አላውቅም*፤ ልክ እንደ ሙሴ (ዘፀ4፥10)፣ ኤርምያስም ለነቢይነት ብቃት እንዳልነበረው ይገልጻል፤ ይሁን እንጂ እግዚአብሔር ለእርሱ እንዲናገርለት አድርጎ አቁሞታል (15፥19)። *ገና ትንሽ ልጅ፤* 1ነገ3፥7 ይመ። ኤርምያስ ያሳየውን ፍርሀት ጌታ ወዲያው ሽሮታል (ቍ7)።

*1፥7፤* እግዚአብሔር የጠራ ከሆነ፣ ልጅነትና አለማወቅ ምክንያት ሆነው ሐሳቡን ሊያስቀይሩ አይችሉም (1ጢሞ4፥12 ይመ)፤ እርሱ የጠራቸውን ያጸናል፤ ያስታጥቃልም።

1፥8 *አትፍራቸው*፤ 10፥5፤ 30፥10፤ 40፥9፤ 42፥11፤ 46፥27-28፤ 51፥46 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ35፥4 እና ማብ፤ 4፥10 ይመ። *እኔ ... ከአንተ ጋር ነኝና፤* ቍ 19፤ 15፥20 ይመ። የማይታዘዝን ነቢይ ፍርሀት፣ እግዚአብሔር የሚሰጠው ተስፋና የማያቋርጥ ጥበቃው ማስወገድ አለበት (ዘፀ3፥12 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ26፥3 ማብ ይመ)። *አድንህ ዘንድ*፤ ቍ19፤ 15፥20፤ 39፥17 ይመ። ኤርምያስ እንደማይሰደድ ወይም እንደማይታሰር እግዚአብሔር ቃል አልገባለትም፤ ነገር ግን የከፋ አካላዊ ጒዳት እንደማይደርስበት ገልጾለታል።

1፥9 *አፌን ዳሰሰና፤* ይህ የሆነው በራእይ (የቍ11 ማብ ይመ) ወይም የአነጋገር ዘይቤ ሊሆን ይችላል፤ በሁለቱም መንገድ ሊሆን ይችላል (ከኢሳ6፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቃሌን በአፍህ አኑሬአለሁ፤* ቀደም ሲል በዚሁ ቍጥር ላይ የተጀመረው የአነጋገር

አኑሬአለሁ፤ [10]እንግዲህ፣ እንድትነቅልና እን ድታፈርስ፣ እንድታጠፋና እንድ ትገለብጥ፣ እንድታንጽና እንድትተክል በአሕዛብና በመ ንግሥታት ላይ ዛሬ ሾምሁህ።”

[11]*የእግዚአብሔር ቃል*፣ “ኤርምያስ ሆይ፣ ምን ታያለህ’ ” ሲል ወደ እኔ *መጣ*።

እኔም፣ “የለውዝ በትር አያለሁ” አልሁ።

[12]*እግዚአብሔርም*፣ “ትክክል አይተሃል፤ ቃሌን እፈጽመው ዘንድ እተጋለሁና”[a] አለኝ።

[13]*ዳግመኛም የእግዚአብሔር ቃል*፣ “ምን ታያለህ?” ሲል ወደ እኔ *መጣ*።

እኔም፣ “አንድ የሚፈላ ማሰሮ አያለሁ፤ አፉም ከሰሜን ወደዚህ ያዘነበለ ነው” አልሁ።

[14]*እግዚአብሔርም* እንዲህ አለኝ፤ “ከሰሜን በምድሪቱ በሚኖሩ ሁሉ ላይ ድንገት መዓት ይወርድባቸዋል። [15]እነሆ፤ የሰሜን መን ግሥታትን ሕዝቦች ሁሉ እጠራለሁ” ይላል *እግዚአብሔር*፤

“ንጉሦቻቸው ይመጣሉ፤
ዙፋናቸውን በኢየሩሳሌም መግቢያ
በሮች፣
በቅጥሮቿ ዙሪያ ሁሉ፣
በይሁዳም ከተሞች ሁሉ ይዘረጋሉ።

[16]እኔን በመተው ክፋት ስለ ሠሩ፣
ለሌሎች አማልክት ዕጣን ስላጠኑ፣
እጆቻቸው የሠሯቸውን ስላመለኩ፣
በሕዝቤ ላይ ፍርድን ዐውጃለሁ።

[17]“አንተ ግን ወገብህን ታጠቅ፤ ተነሥ ተህም ያዘዝሁን ሁሉ ንገራቸው፤ አትፍራ ቸውም፤ አለዚያ በፊታቸው አስፈራሃለሁ። [18]እነሆ፤ ዛሬ በመላዪቱ ምድር ላይ አስነ ሣሃለሁ ይኸውም የይሁዳን ነገሥታት፣ አለ ቆቿን፣ ካህናቷንና የምድሪቱን ሕዝብ ሁሉ መቋቋም እንድትችል የተመሸገ ከተማ፣ የብረት ምሰሶና የናስ ቅጥር አድርጌሃ ለሁ። [19]ይዋጉሃል፤ ዳሩ ግን አድንህ ዘንድ እኔ ከአንተ ጋር ነኝና አያሸንፉህም” ይላል *እግዚአብሔር*።

## የእስራኤል ሕዝብ አምላኩን መተው

**2** *የእግዚአብሔር ቃል* እንዲህ ሲል ወደ እኔ *መጣ*፤

[2]“ሂድና ጮኸህ ይህን ለኢየሩሳሌም ጆሮ
አሰማ፤
“*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
‘በወጣትነትሽ ጊዜ የነበረሽን ታማኝነት፣

[a]12 *እተጋለሁ* ለሚለው የዕብራይስጡ አነባብ *የለውዝ በትር* ከሚለው ጋር ይመሳሰላል።

1፥10 ኤር 25፥17፤ 46፥1፤ 12፥17፤ 18፥7-10፤24፥6፤ 31፥4:28
1፥11 ኤር24፥3፤ አሞ7፥8
1፥12 ኢዮ29፥2፤ ኤር44፥27
1፥13 ኤር24፥3፤ዘካ 4፥2፤5፥2
1፥14 ኢሳ14፥31
1፥15 ኤር4፥16፤ 9፥11፤10፥22
1፥16 ዘዳ6፥5፤ዘፀ 20፥3፤ዘኍ25፥3፤መዝ 115፥4-8፤135፥15፤ ኤር2፥13፤4፥12፤7፥9፤ 17፥13፤19፥4፤44፥3:5
1፥17 ቍ7፤ዘዳ31፥ 6፤2ነገ1፥15ኤር7፥27 ፤26፥2:15፤42፥4
1፥18 ኢሳ50፥7
1፥19 ቍ8፤ዘዳ26፥ 3፤መዝ129፥2፤ምሳ20 ፥22፤ኢሳ43፥2፤ኤር 20፥11፤ሐሥ26፥17
2፥1 ኢሳ38፥4፤ሕዝ 1፥3፤ሚክ1፥1
2፥2 ዘፀ13፥21፤ዘዳ 1፥19፤መዝ71፥17፤ ኢሳ54፥4፤ኤር3፥4 ፤ሕዝ16፥8-14:60፤ ሆሴ2፥15፤11፥1፤ራእ 2፥4፤

ዘይቤ እየቀጠለ ሲሆን፣ በጌታና በነቢያቱ መካከል ያለውን ግንኙነት በተለመደና በማይሻር አባባል ይገልጻል (5፥14፤ ዘፀ 4፥15፤ ዘኍ22፥38፤23፥5:12:16፤ ዘዳ18፥18፤ ኢሳ51፥16 ይመ፤ ከ2ጴጥ1፥21 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥10 *ሾምሁሁ*፤ የቍ5 ማብ ይመ። *እንድትነቅልና እንድታፈርስ፣ እንድታጠፋና እንድትገለብጥ፣ እንድታንጽና እን ድትተክል*፤ 12፥14-15:17፤ 18፥7-10፤ 24፥6፤ 31፥28፤ 42፥10፥ 45፥4 ይመ። የመጀመሪያዎቹ ሁለት ጥንድ ግሦች ኤርምያስ ስለ ጨለማ ዘመን የሚተነብይ ነቢይ እንደ ሆነ በአጽንዖት የሚያ መለክቱ ሲሆኑ፣ የመጨረሻው አንድ ጥንድ ደግሞ የመመለስና እንደ ገና የመታደስ ነቢይ እንደ ሆነ ያመለክታል። መመለስና መጠገን ቢኖርም ይህ በሁለተኛ ደረጃ የሚሆን ነበር። የመጀመ ሪያው ግሥ “መንቀል”ና የመጨረሻው ግሥ፣ “መትከል” ተቃራ ኒዎች ናቸው፤ ሌሎች (“ማፍረስ”፣ “ማጥፋት”፣ “መገልበጥ”) ደግሞ የ“ማነጽ” ተቃራኒዎች ናቸው።

1፥11 *ምን ታያለህ?* ትንቢት ለማመልከትና የሚታየውን ራእይ ለማገናዘብ እግዚአብሔር ወይም አገልጋዮቹ ብዙ ጊዜ የሚያ ሰሙት አባባል ነው (ቍ13፤ አሞ7፥8፤8፥2፤ ዘካ4፥2፤5፥2 ይመ)።

1፥12 *እተጋለሁና*፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጥ ቃል “የለውዝ በትር” ከሚለው አባባል ጋር ተመሳሳይ ድምፅ አለው። የለውዝ ተክል (ቍ11) በዓመቱ መጀመሪያ እንደሚያብብ (ስለ ዚህ ቀድሞ “እንደሚነሣ”፣ “መትጋት” ለተባለው የገባውም የዕብ ራይስጥ ቃል “ንቁ” ማለት ነው)፣ እግዚአብሔርም ቃሉን ከፍጻሜው ለማድረስ ወይም ከፍጻሜ ሲደርስ ለማየት ምን ጊዜም ነቅቶ ይጠ ብቃል።

*1፥13፤ ማሰሮ*፤ ይህ ቃል ኢዮ41፥31 ላይ “ምንቸት” ተብሎ ተተርጕሞአል፤ ይህም መጠኑ ትልቅ መሆኑን የሚያመ ለክት ነው (ሕዝ24፥3-5 ይመ)።

*1፥14፤ ከሰሜን ... መዓት*፤ የኢሳ41፥25 ማብ ይመ። *ይወርድባቸዋል*፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በቍ13 ላይ “የሚፈላ” ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ ድምፅ አለው። ይህ ግስ ብዙውን ጊዜ “መከፈት” ማለት ቢሆንም፣ በኢሳ14፥17 ላይ “መስደድ” ተብሎ ተተርጕሞአል፤ ይህ ትርጕም በዚህ ቍጥር ላይ ካለው ጋር ተቀራራቢ ፍቺ አለው። *ምድሪቱ፤* በይሁዳ ምድር ማለት ነው (ቍ15 ይመ)።

1፥15 *የሰሜን መንግሥታትን*፤ አሹርባኒፓል በ627 ዓ.ቅ. ክ ከሞተ በኋላ፣ የአሦር መንግሥት ለእስራኤል አሥጊነቱ እምብዛም ስለ ነበር፣ “የሰሜን መንግሥታት” ሲባል ባቢሎንንና ተባባሪዎቿን የሚያመለክት ነው። *ዙፋናቸውን በኢየሩሳሌም መግቢያ በሮች ... ይዘረጋሉ፤* ይህ ትንቢት ስለ መፈጸሙ፣ 39፥3 ይመ። የከተማ መግቢያ በር አስተዳዳሪዎች ተሰብስበው ብያኔ የሚሰጡበት ስፍራ በመሆኑ (የዘፍ19፥1፤ የሩት4፥1 ማብ ይመ)፣ ባቢሎናውያን የይሁዳን የዘውድ አገዛዝ ባለሥልጣናት በራ ሳቸው ሹሞች ተኳቸው (ከ43፥10፤ 49፥38 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥16 *በሕዝቤ ላይ ፍርድን*፤ በሕዝቡ ላይ ሥልጣን ያለው አምላክ፣ ስለ ኀጢአታቸው በገዛ ሕዝቡ ላይ ይፈርዳል፤ ፍርዱን በተግባር ላይ ለማዋልም ባቢሎናውያንን እንደ መሣሪያ ይጠቀ ማል። *ለሌሎች አማልክት ዕጣን ስላጠኑ፤* በአረማውያን ዘንድ የተለመደ ባዕድ አምልኮ ነው (ለምሳሌ 7፥9፤ 11፥12-13:17፤ 18፥15፤ 19፥13፤ 32፥29፤ 44፥17)። *እጆቻቸው የሠሯቸውን*፤ የ ተቀረጹ የጣዖታት ምስሎችን ነው (16፥19-20፤ 25፥6፤ 2ነገ 22፥17፤ 2ዜና33፥22፤ ኢሳ46፥6 ይመ)።

1፥17 *አንተ ግን ወገብህን ታጠቅ*፤ ተዘጋጅ ለማለት ነው። ተመሳሳይ አባባሎችን በዘፀ12፥11፤ በ1ነገ18፥46፤ በ2ነገ 4፥29፤ 9፥1፤ በኢዮ38፥3፤ 40፥7 ላይ ይመ።

1፥18 *የተመሸገ ከተማ፤* የአለመደፈርና የአለመነካት ምልክት ነው (5፥17፤ ምሳ18፥11:19 ይመ)። *የብረት ምሰሶና*፤ በብሉይ ኪዳን ውስጥ እዚህ ላይ ብቻ የተጠቀሰ አባባል ሲሆን፣ አባባሉም የክብርና የብርታት መግለጫ ነው። የናስ ቅጥር፤ 15፥20 ይመ። ኤርምያስ እግዚአብሔር በሰጠው አገልግሎት ላይ ስድብና ስደት ሊደርስበት ይችላል፤ ጠላቶቹ ራሳቸው “ናስና ብረት” ሆነው ቢመጡበትም (6፥28)፣ የመቋቋም ችሎታ አለ ው። *ነገሥታት፣ አለቆቿን ካህናቷንና ... ሕዝብ*፤ ነቢዩንና አምላኩን ሕዝቡ በሙሉ ይቃወማሉ (ለምሳሌ 2፥26፤ 23፥8፤ 32፥32 ይመ)።

*1፥19፤* የቍ8 ማብ ይመ፤ በተጨማሪ 15፥20 ይመ።

*2፥1-6፥30፤* እነዚህ ምዕራፎች በኢዮስያስ ዘመነ መንግ ሥት (3፥6) ኤርምያስ ገና በመጀመሪያው የአገልግሎቱ ጊዜ የተናገራቸው እንደ ሆኑ ይታመናል። የክፍሉ መሠረታዊና ማእከላዊ ሐሳብ፣ የይሁዳ ሕዝብ በጠቅላላ በእግዚአብሔር ላይ የነበረውን እምነት ትቶ ወደ ኋላ መመለሱን የሚጠቍም ነው (ም2-5)፤ ይህም የማይቀረውን የእግዚአብሔርን የበቀል ቅጣት አስከትሎአል፤ ቍጣው የተገለጠውም ባዕዳን ነገሥታትን በሕዝቡ ላይ በማምጣትና በማስወረር ነበር (ም6)።

*2፥1-3፥5፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ ዐመፅና ወደ ኋላ ማፈ ግፈግ በተለያዩ የአነጋገር ዘይቤዎችና ምሳሌዎች ተገቢ በሆነ የሥነ ጽሑፍ ስልት በሚገባ ተብራርቶአል።

*2፥1፤* የ1፥2 ማብ ይመ።

2፥2 *ታማኝነት*፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጥ ቃል በሁለት

በሙሽርነትሽም ወራት እንዴት እንደ
ወደድሽኝ፣
በምድረ በዳ ዘር በማይዘራበት ምድር፣
እንዴት እንደተከተልሽኝ አስታውሳለሁ::
[3]እስራኤል ለእግዚአብሔር ቅዱስ ነበረች፤
የመከሩም በኵር ነበረች፤
የዋጧት ሁሉ በደለኞች ሆኑ፤
መዓትም ደረሰባቸው' "
ይላል እግዚአብሔር::
[4]የያዕቆብ ቤት ሆይ፤
የእስራኤል ቤት ወገን ሁላችሁ፣ የእግዚ
አብሔርን ቃል ስሙ::
[5]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"አባቶቻችሁ ከእኔ የራቁት፣
ከንቱ ነገርን የተከተሉት፣
ራሳቸውም ከንቱ የሆኑት፣
ምን ጥፋት አግኝተውብኝ ነው?
[6]እነርሱም፣ 'ከግብፅ ምድር ያወጣን፣
በወና ምድረ በዳ፣
በጐድጓዳና በበረሓ መሬት፣
በደረቅና በጨለማ* ቦታ፣
ሰው በማያልፍበትና በማይኖርበት ስፍራ፣
የመራን እግዚአብሔር ወዴት ነው?'
ብለው አልጠየቁም::
[7]እኔ፣ ፍሬዋንና በረከቷን እንድትበሉ፣
ለም ወደ ሆነ መሬት አመጣኋችሁ፤
እናንተ ግን መጥታችሁ ምድሬን
አረከሳችሁ፤
ርስቴንም ጸያፍ አደረጋችሁ::
[8]'እግዚአብሔር ወዴት ነው?' ብለው፣
ካህናቱ አልጠየቁም፤
ከሕጉ ጋር የሚውሉት አላወቁኝም፤
መሪዎቹ ዐመፁብኝ፤
ነቢያቱም በበኣል ስም ተነበዩ፤
ከንቱ ነገሮችን ተከተሉ::
[9]"ስለዚህ እንደገና ከእናንተ ጋር እፋረዳለሁ፣"
"ከልጅ ልጆቻችሁም ጋር እከራከራለሁ::
ይላል እግዚአብሔር::
[10]ወደ ኪቲም* ጠረፍ ተሻገሩና እዩ፤
ወደ ቄዳርም* ልካችሁ በጥንቃቄ
መርምሩ፣
እንዲህ ዐይነት ነገር ተደርጎ ያውቅ
እንደሆነ ተመልከቱ፤

2፥3 ዘፀ19፥6፤ዘሌ 23፥9-14፤ዘዳ7፥6፤ኢሳ41፥11፤ኤር10፥25፤30፥16፤50፥7፤ያዕ1፥18፤ራእ14፥4፤
2፥5 ዘዳ 32፥21፤ 1ሳሙ12፥21፤2ነገ 17፥15፤መዝ31፥6
2፥6 ዘፀ6፥6፤ዘዳ 1፥19፤32፥10፤ኤር 51፥43፤ሆሴ13፥4
2፥7 ዘኍ13፥27፤ ዘዳ8፥7-9፤11፥10-12፤ መዝ106፥34-39፤ኤር 3፥9፤7፥30፤16፥18፤ ሕዝ11፥21፤36፥17
2፥8 ቍ25፤1ሳሙ 2፥12፤1ነገ18፥22፤ ኢሳ40፥19፤56፥10፤ ኤር3፥15፤4፥22፤5፥1 9፤9፥14፤16፡19፤22፥9 ፤23፥1፤25፥34፤50፥6፤
2፥9 ኤር25፥31፤ ሆሴ4፥1፤ሚክ 6፥2
2፥10 ዘፍ10፥4፤ 25፥13

*6 ወይም በሞት ጥላ
*10 ኪቲም- ቆጵሮስና የምዕራባዊ የባህር ዳርቻ ማለት ነው
*10 ቄዳር- በሶርያዊ ዐረቢያ ምድረ በዳ የሚገኙ የበዱይን ነገዶች መኖሪያ

ሰዎች መካከል ወይም በሰውና በእግዚአብሔር መካከል ሊኖር የሚችለውን ፍጹም ታማኝነት፣ ፍቅርንና ቅንነትን የሚያመለክት ነው:: *በወጣትነትሽ ... በሙሽርነትሽም ...፤* እስራኤል በጥንት ታሪኳ ከእግዚአብሔር ጋር የጠበቀና የሚያስቀና ኅብረት ነበራት፤ አምላኳ በዘይቤአዊ አገላለጽ እንደ ባሏ ይቈጠር ነበር (3፥14፤ 31፥32፤ ኢሳ54፥5፤ ሆሴ2፥16):: *እንደ ወደድሽኝ፤* በኋላ ግን በሚያሳዝን ሁኔታ የቀድሞ ፍቅራቸውን በመተው (ከራእ2፥4 ጋር ያነጻጽሩ)፣ "ባዕዳን አማልክትን" ወደው አምላካቸውን ተዉ:: *ተከተልሽኝ፤* ኋላ ግን "ከንቱ ጣዖታትን" (ቍ5:8)፣ "በአሊ ምን" (ቍ23) ተከተሉ:: *ምድረ በዳ፤* የሲና በረሓ ማለት ነው (ቍ6 ይመ)::

2፥3 *ለእግዚአብሔር ቅዱስ፤* ለእርሱ እንዲሁም ለአገልግሎቱ የተለየ ማለት ነው (የዘፀ3፥5፤ የዘሌ11፥44፤ የዘዳ7፥6 ማብ ይመ):: *በኵር፤* ልክ የእስራኤል "የመከር በኵራት ምርጥ" ለእግዚአብሔር ይሰጥ እንደ ነበረው ሁሉ ማለት ነው (ዘፀ23፥19፤ ዘኍ18፥12፤ 2ዜና31፥5፤ ሕዝ44፥30 ይመ)፤ ሕዝቡም ለእግዚ አብሔር እንደዚሁ የመጀመሪያና ምርጥ ገንዘቡ ነው (ከያዕ1፥18፤ ከራእ14፥4 ጋር ያነጻጽሩ):: *መዓትም ደረሰባቸው፤* ለምሳሌ ዘፀ 17፥8-16 ይመ::

2፥4 *ስሙ፤* በትንቢት ነክ ጽሑፎች ሁሉ የተለመደ መለኮታዊ ትእዛዝ ሲሆን፣ የእግዚአብሔርን ሕዝብ እንዲሁም አሕዛብን ጭምር ሕጋዊ ግዴታ እንዳለባቸው ለማስገንዘብ፣ አስፈላጊ ከሆነም በእነርሱ ላይ ፍርድን ለማስተላለፍ የሚቀርብ ጥሪ ነው (ለምሳሌ 7፥2፤ 17፥20፤ 19፥3፤ 21፥11፤ 22፥2:29፤ 31፥10፤ 42፥15፤ 44፥24:26፤ ኢሳ1፥10፤ ሕዝ 13፥2፤ ሆሴ 4፥1፤ አሞ7፥16 ይመ)::

2፥5 *እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤* የእግዚአብሔር ቃል በነቢዩ በኩል የሚገለጥ መሆኑን ለማመልከት፣ በመግቢያ ላይ የሚገኝ አባባል ነው:: አባባሉ በአጋጣሚው ሁሉ በብዛት መጠቀሱ የታወቀ ቢሆንም፣ በሐሳብ አገላለጻቸው ላይ ተጠቅመውበታል ተብለው በስም የሚጠቀሱ ግን:- ኤርምያስ፣ ኢሳይያስ (ለምሳሌ7፥7)፣ ሕዝቅኤል (ለምሳሌ2፥4)፣ አሞጽ (ለምሳሌ1፥3)፣ አብድዩ (1)፣ ሚክያስ (3፥5)፣ ናሆም(1፥12)፣ ሐጌ (ለምሳሌ1፥2)፣ ዘካርያስ (ለምሳሌ1፥3) እንዲሁም ሚልክያስ (1፥4) ናቸው:: *የራቁት፤* 4፥1፤ 23፥13:32፤ 31፥19፤ 50፥6፤ ኢሳ53፥6፤ ሕዝ34፥4-6:16፤ 1ጴጥ2፥25 ይመ:: ከንቱ ነገርን የተከተሉት፤ ቍ8:23 ይመ፤ በተጨማሪ የቍ2 ማብ ይመ:: "ከንቱ" በሚል አባባል ጣዖታትን መጥራትና መግለጽ በኤርምያስ ዘንድ የተለመደ ነው (8፥19፤ 10፥8:15፤ 14፥22፤ 16፥19፤ 51፥18):: *ራሳቸውም ከንቱ የሆኑት፤* 2ነገ17፥15 ይመ:: ጣዖትን የሚያመልኩ ሰዎች፣ ከነዚያ ከጣዖታቱ የሚሻሉ አይደሉም (መዝ115፥8 ይመ)::

2፥6 *ከግብፅ ምድር ያወጣን ... እግዚአብሔር፤* የእስራኤል ታዳጊ የሆነው እግዚአብሔር (የዘፍ2፥4፤ የዘፀ3፥15 ማብ ይመ)፣ እርሱን ብቻ ያገለግሉት ዘንድ ሕዝቡን ከግብፅ ባርነት ነጻ አውጥቶአል (ዘፀ20፥2-6):: *የመራን፤* እረኛ መንጋውን እንደ ሚመራ ማለት ነው (ቍ17፤ ዘዳ8፥15፤ መዝ23፥2-3 ይመ):: *ምድረ በዳ ... በጨለማ ቦታ፤* በረሓ ብዙውን ጊዜ ከጨለማና ከእርሱም ጋር ተያይዘው ከሚገኙ ነገሮች ጋር ከመተሳሰሩም በላይ፣ እነዚህኑ ለመሰሉ ነገሮች በትእምርትነት ለማስየት የቆመ ምሳሌያዊ አባባል ነው (ቍ31፤ 9፥10፤ 12፥12፤ 17፥6፤ 23፥10፤ መዝ44፥19)::

2፥7 *ለም፤* ለዚህ ቃል የሚገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል "ካርሜል" የሚል ሲሆን፣ በ48፥33 ላይ "የአትክልት ቦታ" ተብሉ ተተርጕሞአል፤ በሌላ ቦታ ደግሞ የስፍራ ስም ሆኖ ገብቶአል (ኢሳ33፥9 እና ማብ ይመ):: በ4፥26 ላይም "ፍሬያማ ምድር" ተብሉ ሲገለጽ፣ የምድረ በዳ ተቃራኒ ሆኖ ገብቶአል:: *ምድሬን አረከሳችሁ፤* ከእምነታቸው ሥርዐት አኳያ ሲታይ አጕድፈውታል (3፥1-2:9፤ 16፥18፤ የዘሌ4፥12 ማብ ይመ):: *ርስቴንም፤* እግዚአብሔር ለእስራኤል ሕዝብ ያወረሳቸውን ከራሳቸው ጋር የተቈራኘው የተስፋ ምድር ነው (በተለይ 12፥7-9:14-15 ተመ):: *ጸያፍ፤* የዘሌ7፥21 ማብ ይመ::

*2፥8፤* የትኛውም ወገን እግዚአብሔርን ለመጠየቅ ፈቃደኛ አልነበረም (ቍ6 ይመ):: *ካህናቱ ... መሪዎቹ ... ነቢያቱም፤* የ1፥18 ማብ ይመ:: ከሕጉ ጋር የሚውሉት፤ ካህናት ናቸው (ዘዳ31፥11 እና ማብ ይመ):: *መሪዎቹ፤* የዕብራይስጡ ቃል በቁሙ ሲታይ "እረኞች" የሚል ትርጓሜ ይኖረዋል፤ ይኸው ቃል በሌላ ስፍራ ገዦችን ያመለክታል (23፥1-4፤ 49፥19፤ 50፥44፤ በተለይ ሕዝ 34፥1-10:23-24 ይመ):: *በበኣል፤* በበኣል ስም ለማለት ነው (ከ11፥21፤ 14፥15፤ 23፥25፤ 26፥9 ጋር ያነጻጽሩ):: *ከንቱ፣* የዕብራይስጡ ቃል በቁሙ ሲታይ "ፋይዳ ቢስ" የሚል ትርጓሜ አለው (ቍ11 ይመ፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ቍ5 ላይ ካለው ቃል ጋር አንድ ባይሆንም፣ ትርጕሙ ተመሳሳይ ነው )::

2፥9 *እፋረዳለሁ፤* የቍ4 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 25፥31፤ ሆሴ4፥1፤ 12፥2፤ ሚክ6፥2 ይመ::

*2፥10፤ ኪቲም፤* ከይሁዳ ምድር በስተ ምዕራብ የነበሩትን አገሮችና ቦታዎች የሚያመለክት ነው:: *ቄዳርም፤* ከይሁዳ በስተ ምሥራቅ የነበሩትን አገሮችና ቦታዎች ያመለክታል:: ይህ አካባቢ የበደዊ ነገድ መኖሪያ ሲሆን፣ በሦርያ ዐረብ ምድረ በዳ ውስጥ ይገኛል (49፥28፤ ኢሳ21፥16 እና ማብ ይመ)::

[11]የእውነት አማልክት ባይሆኑም እንኳ፣
አማልክቱን የለወጠ ሕዝብ አለን?
ሕዝቤ ግን ክብራቸው[ሠ] የሆነውን፣
በከንቱ ነገር ለወጡ::
[12]ሰማያት ሆይ፤ በዚህ ተገረሙ፤
በታላቅ ድንጋጤም ተንቀጥቀጡ፤"
ይላል እግዚአብሔር::
[13]"ሕዝቤ ሁለት ኀጢአት ፈጽመዋል፣
ሕያው የውሃ ምንጭ የሆንሁትን፣ እኔን ትተዋል፤
ውሃ መያዝ የማይችሉትን ቀዳዳ የውሃ
ማጠራቀሚያ ጉድጓዶች፣
ለራሳቸው ቈፍረዋል::
[14]እስራኤል ባሪያ ነውን? ወይስ የቤት
ውልድ ባሪያ?
ታዲያ፣ ስለምን ለብዝበዛ ተዳረገ?
[15]አንበሶች በእርሱ ላይ አገሡ፤
በኀይለኛ ድምፅም ጮኹበት::
ምድሩን ባድማ አድርገውበታል፤
ከተሞቹ ተቃጥለዋል፤ ወናም ሆነዋል::
[16]ደግሞም የሜምፎስና[ረ] የጣፍናስ ሰዎች፣
መኻል እናትሽን ላጩሽ::[ሰ]
[17]በመንገድ የሚመራሽን፣
እግዚአብሔር አምላክሽን በመተውሽ፣
ይህን በራስሽ ላይ አላመጣሽምን?

2፥11 ኢሳ37፥19፤ ኤር16፥20፤1ሳሙ4፥21፤ሮሜ1፥23፤ገላ4፥8
2፥13 ዘዳ31፥16፤ ኢሳ12፥3፤65፥11፤ ዮሐ4፥14
2፥14 ዘፀ4፥22፤ኤር31፥9
2፥15 ዘሌ26፥43፤ ኢሳ1፥7፤2ነገ25፥9፤ ኤር4፥7፤50፥17
2፥16 ኢሳ19፥13፤ ኤር43፥7-9
2፥17 ኢሳ1፥28፤ ኤር4፥18፤17፥13፤ 19፥4
2፥18 ኢሱ13፥3፤ 2ነገ16፥7፤ኢሳ7፥20፤ 30፥2፤ሆሴ5፥13፤7፥11፤8፥9
2፥19 ኢዮ20፥14፤ መዝ36፥1፤ኢሳ3፥9፤ 59፥12፤ኤር3፥11:22፤ 7፥24፤11፥10፤14፥7፤ 19፥4፤ሆሴ5፥5፤14፥4፤ አሞ 8፥10፤
2፥20 ዘሌ26፥13፤ ዘዳ12፥2፤ኢዮ21፥14፤ መዝ2፥3፤ኢሳ1፥21፤ 57፥7፤ኤር3፥23፤5፥5፤ 17፥2፤ሕዝ16፥15
2፥21 ዘፀ15፥17፤ መዝ80፥8፤ኢሳ5፥4

[18]ከሺሖር[ሸ] ወንዝ ውሃ ለመጠጣት፣
አሁንስ ለምን ወደ ግብፅ ወረድሽ?
ከኤፍራጥስ ወንዝስ ውሃ ለመጠጣት፣
ወደ አሦር መውረድ ለምን አስፈለገሽ?
[19]ክፋትሽ ቅጣት ያስከትልብሻል፤
ክህደትሽም ተግሣጽ ያመጣብሻል፤
እግዚአብሔር አምላክሽን ስትተዪ፣
እኔንም መፍራት ችላ ስትዪ፣
ምን ያህል ክፉና መራራ እንደሚሆንብሽ፣
እስቢ፤ እስቲ አስተውዪ፤"
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር::
[20]"ከጥንት ጀምሮ ቀንበርሽን ሰበርሁ፤
እስራትሽን በጣጠስሁ፤
አንቺም፣ 'አላገለግልህም!' አልሽ፤
ከፍ ባለውም ኰረብታ ሁሉ ሥር፣
በያንዳንዱም ለምለም ዛፍ ሥር፣
ለማመንዘር ተጋደምሽ::
[21]እኔ፣ እንደ ምርጥ የወይን ተክል፣
ጤናማና አስተማማኝ ዘር አድርጌ
ተክዬሽ ነበር፤
ታዲያ ብልሹ የዱር ወይን ተክል ሆንሽ፣

ሠ11 የዕብራውያን የጥንት ጸሐፍት ትውፊት የሆነው የማሶሬቲክ ጽሑፍ *ክብሬን* ይላል
ረ16 *ሜምፎስ* በዕብራይስጡ *ኖፍ* ይላል ወይም *ጭንቅላትሽን ፈጠፈጡ /ሰነጠቀ* ሰ
ሸ18 የዐባይ ወንዝ አንዱ ተነጣይ ጅረት ነው

2፥11 *አማልክቱን ... አለን?* አሉታዊ መልስ ለማግኘት የቀረበ ጥያቄ ሲሆን፣ ይሁዳ አምላኳን እግዚአብሔርን ትታ ባዕዳን አማልክት መከተሏ ምን ያህል አስገራሚ መሆኑን ለማሳየት የተሰነዘረ ጥያቄ ነው:: *ክብራቸው የሆነውን፤* እግዚአብሔርን ነው (መዝ106፥20፤ ሆሴ4፥7፤ 1ሳሙ15፥29 ይመ):: *ከንቱ፤* የቍ8 ማብ ይመ::

2፥12 *ሰማያት ሆይ ... ተገረሙ፤* የኢሳ1፥2 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ሚክ6፥1-2 እና ማብ ይመ::

*2፥13፤* 1፥16 ይመ:: *ሕያው የውሃ ምንጭ የሆንሁትን፣ እኔን፤* 17፥13 ይመ:: ለሕይወት የሚሆን በረከትን ለሕዝቡ የሚሰጥ እግዚአብሔር ራሱ ነው (መዝ36፥9 ይመ፤ በተጨማሪ የዮሐ4፥10 ማብ፤ ኢሳ55፥1 እና ማብ፤ ራእ21፥6 ይመ):: *ቀዳዳ የውሃ ማጠራቀሚያ ጉድጓዶች፤* የውሃ ማጠራቀሚያ ጉድጓዶች ውሃ ይዘው እንዲቈዩ ውስጣቸው ውሃ በማያሠርግ (በማያስተላልፍ) ፕላስተር ይለበድ ነበር:: ጣዖታት፣ ልክ እንደ ተበሳሳ የውሃ ማጠራቀሚያ ጉድጓድ፣ ለሚያመልኳቸው አስተማማኝነት የላቸውም፤ እግዚአብሔር ግን ዘወትር ሕይወትን አትረፍርፎ ይሰጣል፤ ታማኝነቱም ለዘላለም ነው::

2፥14 *እስራኤል ... ባሪያ?* ይህም አሉታዊ መልስ ለመስጠት የሚጋብዝ ጥያቄ ነው (የቍ11 ማብ ይመ)፤ ጥያቄው አሉታዊ መልስ የሚገባው እግዚአብሔር በዘፀአት ላይ በተገለጸው ታሪክ ውስጥ ከፈጸመው የመቤዠትና ነጻ የማውጣት ሥራ አንጻር ሲታይ ነው (ዘፀ6፥6፤ 20፥2 ይመ):: *ለብዝበዛ፤* ለአሦርና ለግብፅ ምርኮኛ መሆናቸውን ለማመልከት ነው (ቍ15-16 ይመ)::

2፥15 *አንበሶች፤* ምናልባት በቀሙ አንበሶችን ማለቱ ይሆናል (2ነገ17፥25-26 ይመ)፤ እዚህ ላይ ግን አሦርን ለማመልከት የገባ ይመስላል (ቍ18፤ 50፥17፤ የ4፥7፤ የኢሳ15፥9 ማብ ይመ):: *አገሡ ... በኀይለኛ ድምፅም ጮኹበት፤* አሞ3፥4 ይመ:: *ምድሩን ባድማ አድርገውበታል፤* 4፥7፤ 18፥16፤ 50፥3 ይመ:: *ከተሞቹ ተቃጥለዋል፤ ወናም ሆነዋል፤* ይህ ሐረግ በዕብራይስጡ አባባል ሲታይ ከ4፥7 ጋር በጣም ይመሳሰላል፤ በ4፥7 ያለው፣ "ከተሞችሽ ፈራርሰው ይወድቃሉ፤ ያለ ነዋሪም ይቀራሉ" ይላል (ከ22፥6 ጋር ያነጻጽሩ)::

2፥16 *የሜምፎስ፤* 44፥1፤ 46፥14:19 ይመ:: በተጨማሪም የኢሳ19፥13 ማብ ይመ:: *የጣፍናስ፤* ምናልባት በአሁኑ ዘመን 'ቴል ዴፍነህ' በመባል የሚታወቀውና 'መንዛሌህ' ከተባለው ሐይቅ በስተ ደቡብ፣ በምሥራቁ የዐባይ ወንዝ ባሕር መግቢያ የሚገኘው፣ ግሪኮች ኋላ 'ዳፍናይ' ብለው የጠሩት የግብፅ ከተማ ሳይሆን አይቀርም (43፥7-9፤ 44፥1፤ 46፥14፤ ሕዝ30፥18 ይመ):: *መኻል ዐናትሽን ላጩሽ፤* ውርደትንና ጉዳት ማድረስን ለመግለጽ የገባ የአነጋገር ዘይቤ ነው (47፥5፤ 48፥37፤ በተጨማሪም የኢሳ3፥17፤ 7፥20 ማብ ይመ)::

2፥17 *የሚመራሽን፤* የቍ6 ማብ ይመ:: *በመንገድ፤* ዘፀ 18፥8፤ 23፥20፤ ዘዳ1፥33 ይመ::

*2፥18፤* ቍ36 ይመ:: እስራኤል ወይም ይሁዳ አንድ ጊዜ ከግብፅ፣ ሌላ ጊዜ ደግሞ ከአሦር ድጋፍ መሻታቸው፣ በኤርምያስ ዘመን ብቻ የታየ ዝንባሌ አልነበረም (ለምሳሌ ሆሴ7፥11፤ 12፥2 ይመ):: *ውሃ ለመጠጣት፤* ውሃው ምንም ይሁን ምን ከእግዚአብሔር ይልቅ ከጠላቶቿ ዘንድ የሚቸራት ነበር (ቍ13፤ ኢሳ8፥6-8 እና ማብ ይመ)::

2፥19 *ክህደትሽም፤* 3፥22፤ 5፥6፤ 14፥7 ይመ፤ ቃሉ፣ በተደጋጋሚ ወደ ክህደት መንሸራተትን የሚያመለክት ነው:: *ክፋትሽ ቅጣት ያስከትልብሻል፤* ኀጢአት ወይም በደል ካለ፣ ተመጣጣኝ ቅጣት መከተሉ የማይቀር ነው፤ ሰው በስሕተት ጐዳና መጓዝ ሲጀምር፣ ያን ጊዜ የእግዚአብሔር ጥበቃ ሊለየው ይጀምራል፤ በረከቱ ይሸሸዋል፤ ለጠላትም የተጋለጠ ይሆናል::

*2፥20-3፥5፤* ይሁዳ በእግዚአብሔር ላይ ያደረገችውን ዐመፅ ኤርምያስ አያሌ የንግግር ዘይቤዎችን በመጠቀም ውብ በሆነ ቋንቋ ይገልጸዋል::

*2፥20፤* ይሁዳ እንደ እልከኛ ተጠማጅ ከብት (ሆሴ4፥16 ይመ) የእግዚአብሔርን ትእዛዛት ላለመጠበቅ እምቢተኛ ሆናለች:: *ቀንበርሽን ሰበርሁ፤ እስራትሽን በጣጠስሁ፤* 5፥5 ይመ፤ በተጨማሪም 31፥18 ይመ፤ ከመዝ2፥3 ጋር ያነጻጽሩ:: ይሁዳ የእግዚአብሔርን ሕግ ጥሳለች፤ ኪዳኑንም አላከበረችም:: *ከፍ ባለውም ኰረብታ ሁሉ ሥር፣ በእያንዳንዱም ለምለም ዛፍ ሥር፤* የአረማውያንን የአምልኮ ቦታዎች ለመመልከት ነው (1ነገ14፥23፤ 2ነገ17፥10፤ሕዝ6፥13 ይመ):: *ለማመንዘር፤* ለባዕድ አምልኮ ሲባል የዝሙት ሥርዐት መፈጸም እጅግ አስጸያፊ ተግባር ነበር (ለምሳሌ ሆሴ4፥10-14 ይመ)::

*2፥21፤* ኢሳ5፥1-7 ይመ፤ በተጨማሪም መዝ80፥8-16፤ሕዝ17፥1-10፤ ሆሴ10፥1-2 ይመ፤ ከዮሐ15፥1-8 ጋር ያነጻጽሩ:: *ምርጥ የወይን ተክል፤* ኢሳ5፥2 ይመ:: ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል እጅግ ልዩ የሆነውንና ጥራት ያለውን የወይን ዘር ያመለክታል:: *የዱር፤* ቃል በቃል "ባዕድ" የሚል ትርጕም አለው:: የእስራኤልን ሕዝብ በተምሳሌት የሚያመለክተው የወይን ተክል፣ የእስራኤልን ጠላቶች ከሚያመለክተው የወይን ተክል ጋር ተመሳሳይ መሆን አይገባውም (ዘዳ32፥32 ይመ)::

እንዴት ተለወጥሽብኝ?
[22]በልዩ ቅጠል ብትታጠቢ፣
ብዙ ሳሙና ብትጠቀሚም፣
የበደልሽ ዕድፍ አሁንም በፊቴ ነው፤”
ይላል ጌታ እግዚአብሔር።
[23]“ ‘አልረከስሁም፣
በኣሊምን አልተከተልሁም’ እንዴት
ትያለሽ?
በሸለቆ ውስጥ ምን እንዳደረግሽ እስቲ
አስቢ፣
ምንስ እንደ ፈጸምሽ ተገንዘቢ፤
እንደምትፋንን ፈጣን ግመል ሆነሻል፤
[24]በምድረ በዳ እንደ ለመደች፣
በፍትወቷ ነፋስን እንደምታነፈንፍ፣
የሜዳ አህያ ነሽ፤
ከመጎምጀቷ ማን ሊገታት ይችላል?
ለሚፈልጓት ሁሉ ያለ ምንም ድካም፤
በፍትወቷ ወራት በቀላሉ ትገኝላቸዋለች።
[25]እግርሽ እስኪነቃ አትሩጪ፤
ጉሮሮሽም በውሃ ጥም እስኪደርቅ
አትቅበዝበዢ።
አንቺ ግን፣ ‘በከንቱ አትድከም፤
ባዕዳን አማልክትን ወድጃለሁ፤
እነርሱን እከተላለሁ’ አልሽ።

[26]“ሌባ በተያዘ ጊዜ እንደሚያፍር፣
የእስራኤልም ቤት አፍሮአል፤
እነርሱ፣ ንጉሦቻቸውና ሹሞቻቸው፣
ካህናታቸውና ነቢያታቸው እንዲሁ
ያፍራሉ።
[27]ዛፉን፣ ‘አንተ አባቴ ነህ’
ድንጋዩንም፣ ‘አንተ ወለድኸኝ’ አሉ፤
ፊታቸውን ሳይሆን፣
ጀርባቸውን ሰጥተውኛልና፤
በመከራቸው ጊዜ ግን፣
‘መጥተህ አድነን!’ ይላሉ።
[28]ታዲያ፣ ለታመልካቸው ያበጀሃቸው
አማልክት ወዴት ናቸው?
በመከራህ ጊዜ ሊያድኑህ የሚችሉ
ከሆነ፣
ይሁዳ ሆይ፤ እስቲ ይምጡና ያድኑህ፤
የከተሞችህን ቍጥር ያህል፣
የአማልክትህም ብዛት እንዲሁ ነውና።
[29]“ለምን በእኔ ታማርራላችሁ?
ያመፃችሁብኝ እናንተ ሁላችሁ ናችሁ፤”
ይላል እግዚአብሔር።
[30]“ልጆቻችሁን በከንቱ ቀጣኋቸው፤
እነርሱም አልታረሙም።
ሰይፋችሁ እንደ ተራበ አንበሳ፣
ነቢያታችሁን በልቶአል።

[31]“የዚህ ትውልድ ሰዎች ሆይ፤ የእግዚ
አብሔርን ቃል አስተውሉ፤
“እኔ ለእስራኤል ሕዝብ ምድረ በዳ፣
ወይስ ድቅድቅ ጨለማ ያለበት ምድር
ሆንሁበትን?
ሕዝቤ፣ ‘እንደ ልባችን ልንሆን
እንፈልጋለን፤
ተመልሰንም ወደ አንተ አንመጣም’
ለምን ይላል?
[32]ለመሆኑ ቆንጆ ጌጣጌጧን፣
ሙሽራ የሰርግ ልብሷን ትረሳለችን?
ሕዝቤ ግን፣
እጅግ ብዙ ቀን ረስቶኛል።

2፥22 ኢዮ9፥30፤ መዝ51፥2፤ኤር17፥1፤ ሰቆ1፥8:17
2፥23 ቍ 25:33፤ ምሳ30፥12፤2ነገ23፥10፤ኤር7፥31፤9፥14፤ 19፥2፤23፥27፤31፥22: 40
2፥24 ዘፍ16፥12፤ ኢዮ39፥6፤ኤር14፥6
2፥25 ቍ8:23፤ዘዳ 32፥16፤ኢሳ57፥10፤ ኤር3፥13፤14፥10
2፥26 ኤር32፥32፤ 44፥17:21፤48፥27፤ ሰቆ1፥7፤ሕዝ16፥54፤ 22፥26፤36፥4
2፥27 መሳ10፥10፤ 1ነገ14፥9፤2ዜና29፥6፤ መዝ14፥3፤ኢሳ26፥16 ፤37፥20፤ኤር3፥9፤10፥ 8፤18፥17፤32፥33፤ሕዝ 7፥22፤8፥16፤ሆሴ 5፥15
2፥28 ዘዳ32፥37፤ 2ነገ17፥29፤ኢሳ 40፥19፤45፥20፤
2፥29 ኤር5፥1፤ 6፥13፤ዳን9፥11፤ሚክ 3፥11፤7፥2
2፥30 ዘሌ26፥23፤ ነህ9፥26፤ኤር11፥21፤ ሐሥ7፥52፤1ተሰ2፥15
2፥31 ኢዮ21፥14፤ ኢሳ 45፥19
2፥32 ዘዳ32፥18፤ ኢሳ 57፥11

2፥22 *በልዩ ቅጠል ... ሳሙና* ‘ልዩ ቅጠል’ የተባለው ከዕፀዋት የተሠራ ነበር። ኀጢአትና በደል ይነጻል፤ ይቅር ይባላል (መዝ51፥2:7፤ ኢሳ1፥18 ይመ)፤ ይህ እውን ሊሆን የሚችለው ግን ኀጢአተኛው ንስሓ ሲገባና ሲናዘዝ ብቻ ነው (ምሳ28፥13 ይመ፤ ከ1ዮሐ1፥7:9 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥23 *አልረከስሁም፤* ‘ረከሰ’ ሲባል ካለው የሃይማኖት ሥርዐት አንጻር ጉድፍ መገኘት ማለት ነው (19፥13 ይመ፤ የዘሌ4፥12 ማብ በተጨማሪ ይመ)። *አልተከተልሁም፤* ‘መከ ተል’ ስለሚለው የቍ2 ማብ ይመ፤ በተጨማሪ ቍ25 ይመ። *በኣሊም፤* 9፥14 ይመ፤ የመሳ2፥11 ማብ በተጨማሪ ይመ። *በሸለቆ፤* ምናልባት የሄኖም ሸለቆ ይሆናል (የኢያ15፥5 ማብ ይመ)፤ የሄኖም ልጅ ሸለቆ በመባልም ይታወቃል (7፥31-32፤ 19፥2:6፤ 32፥35)። *እንደምትፋንን፤* የይሁዳ ሕዝብ በዚህ ፈንታ፣ “ወደ ቀኝ፣ ግራም ሳይሉ” (ዘዳ28፥14) ለእግዚአብሔር መታዘዝ ነበረባቸው።

2፥24 *የሜዳ አህያ፤* የማይለምድና (ዘፍ16፥12 ይመ) የማ ይገራ (ኢዮ39፥5-8 ይመ) እንስሳ ነው። *ምድረ በዳ እንደ ለመደች፤* 14፥6፤ ኢዮ24፥5 ይመ። *እንደምታነፈንፍ፤* አባባሉ የሚገልጸው ተረጋግቶ መጠበቅን ሳይሆን ተሯሩጦ መፈለግን ነው (ሆሴ2፥7:13 ይመ)።

2፥25 *እግርሽ እስኪነቃ፤* መጫሚያዋን እስከ ምትጨርስ ድረስ ነው። *በከንቱ አትድከም፤* 18፥12 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ57፥10 ማብ ይመ። *ባዕዳን አማልክትን ወድጃለሁ፤* በመካ ከላቸው ካለው ኪዳን አንጻር፣ አይሁድ ፍቅር ማሳየት የነበረባ ቸው ለአምላካቸው ለእግዚአብሔር ብቻ ነበር፤ አሁን ግን በተቃ ራኒው በመሄድ ላይ ይገኛሉ (ለምሳሌ ዘዳ 6፥6፤7፥7-13፤ ሆሴ2፥14-3፥1 ይመ)። *እነርሱን እከተላለሁ፤* ቍ23 ይመ፤ በተጨማሪም የቍ2 ማብ ይመ።

2፥26 *በተያዘ ጊዜ እንደሚያፍር፤* ለምሳሌ:- ዘፀ22፥3-4 ይመ። “እንደሚያፍር” የሚለው ቃል በዕብራይስጡ “ውርደትን” የሚያመለክት ሲሆን፣ ለከነዓናውያን ዋነኛ ጣዖት፣ ለበኣል አልፎ አልፎ የሚሰጥ መጠሪያ ነበር (11፥13 እና ማብ፣ ሆሴ 9፥10 ይመ፤ እንዲሁም የመሳ6፥32 ማብ ይመ)። *ንጉሦቻቸውና ሹሞቻ ቸው፣ ካህናታቸውና ነቢያታቸው፤* የ1፥18 ማብ ይመ።

*2፥27፤* ኢሳ44፥13-17 ይመ፤ ከዘዳ32፥6:18፤ ከኢሳ64፥8፤ ከሚል2፥10 ጋር ያገናዝቡ። *መጥተህ አድነን፤* ቍ28 ይመ።

2፥28 *የከተሞችህን ቍጥር ያህል፣ የአማልክትህም ብዛት፤* 11፥13 ይመ፤ ከ1ቆሮ8፥5 ጋር ያነጻጽሩ። በመካከለኛው ምሥራቅ የነበሩ የታወቁ ከተሞች ሁሉ የየራሳቸው ‘ጠባቂ’ የሆኑ፣ ባዕዳን አማልክት ነበሯቸው (ከሐሥ19፥28: 34-35 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ብዙዎቹም ከተሞች በባዕዳን አማልክት ስሞች/ይጠሩ ነበር (ለምሳሌ:- የ1፥1 ማብ ይመ)።

2፥29 *ታማርራላችሁ፤* ከቍ9 ጋር ያነጻጽሩ፤ 12፥1፤ ኢዮ 33፥13 ይመ።

2፥30 *ልጆቻችሁን ... ቀጣኋቸው፤* ከዕብ12፥6 ጋር ያነጻ ጽሩ። *አልታረሙም፤* 5፥3 ይመ። *ሰይፋችሁ ... ነቢያታችሁን በልቶአል፤* ለምሳሌ 26፥20-23፤ 2ነገ21፥16፤ 24፥4 ይመ፤ እንዲ ሁም ነህ9፥26 ይመ።

2፥31 *ትውልድ፤* የዚህ ቃል አገባብ ብዙውን ጊዜ በጎ ሁኔታን አያመለክትም (ለምሳሌ:- ዘዳ32፥5 ይመ)። *እኔ ... ምድረ በዳ ... ድቅድቅ ጨለማ ያለበት ምድር ሆንሁበትን?* ከዚህ በተቃራኒ እግዚአብሔር ሕዝቡን በምድረ በዳና በጨለ ማው መካከል እየመራ አሳልፎአል (ቍ6)። “ድቅድቅ ጨለማ” የተባለው “የእግዚአብሔር ጨለማ” ከሚለው ከዕብራይስጡ ሐረግ የተተረጐመ ነው፤ ይህም፣ “ከእግዚአብሔር ዘንድ የተላከ ጨለ ማ” ለማለት ነው (ከ1ሳሙ26፥12 ጋር ያነጻጽሩ)። በማሕ 8፥6 ላይ፣ “ብርቱ ነበልባል” ተብሎ የተተረጐመውም በዕብራይስጡ፣ “የእግዚአብሔር ነበልባል” የሚል ነው።

*2፥32፤* ኢሳ49፥15:18 እና ማብ ይመ። *ሙሽራ፤* ከቍ2 ጋር ያነጻጽሩ። *ሕዝቤ ... ረስቶኛል፤* 18፥15 ይመ፤ እንዲሁም

[33]በፍትወት ለማጥመድ እንዴት ስልጡን
ነሽ?
ልክስክስ ክፉ ሴቶች እንኳ ከመንገድሽ
ብዙ ክፋት ይማራሉ::
[34]በስርቆት ያልያዝሻቸው፣
የንጹሓን ድኾች ደም፣
በልብስሽ ላይ ተገኝቶአል::
ይህን ሁሉ አድርገሽም፣
[35]'እኔ ንጹሕ ነኝ፤
በእርግጥ ቍጣው ከእኔ ርቆአል'
ትያለሽ::
እኔ ግን እፈርድብሻለሁ፤
'ኀጢአት አልሠራሁም' ብለሻልና::
[36]መንገድሽን እየለዋወጥሽ፣
ለምን ትሮጫለሽ?
አሦር እንዳዋረደሽ፣
ግብፅም እንዲሁ ያዋርድሻል::
[37]የታመንሽባቸውን እግዚአብሔር
ስላዋረደ፣
በእነርሱም ስለማይከናወንልሽ፣
እጆችሽን በራስሽ ላይ አድርገሽ፣
ከዚያም ትወጫለሽ::

3 "ሰው ሚስቱን ቢፈታ፣
እርሷም ሄዳ ሌላ ሰው ብታገባ፣
ወደ እርሷ ይመለሳልን?
ምድሪቱስ ፈጽማ አትረክስምን?
አንቺ ግን ከብዙ ወዳጆችሽ ጋር
አመንዝረሻል፤
ታዲያ አሁን ወደ እኔ መመለስ
ትፈልጊያለሽን?"
ይላል እግዚአብሔር::

[2]"እስቲ ቀና ብለሽ ጭር ያሉትን
ኰረብቶች ተመልከቺ፣
በርኵሰት ያልተጋደምሽበት ቦታ
ይገኛልን?
በበረሓ፣ እንደ ተቀመጠ ዘላን ዐረብ፣
በየመንገዱ ዳር ተቀምጠሽ
ወዳጆችሽን ጠበቅሽ::
በዝሙትሽና በክፋትሽ፣
ምድሪቱን አረከስሽ::
[3]ስለዚህ ካፊያ ተከለከለ፤
ኋለኛው ዝናብም ጠፋ::
አንቺ ግን አሁንም የጋለሞታ ገጽታ
አለብሽ፤
ዐይንሽን በዕፍረት አልሰብር ብለሻል::
[4]አሁንም ወደ እኔ ተጣርተሽ፣
'አባቴ፣ የልጅነት ወዳጄ፣
[5]ሁልጊዜ ትቈጣለህን?
ቍጣህስ ለዘላለም ነውን?' አላልሽኝም?
የምትናገሪው እንዲህ ነው፤
ይሁን እንጂ የቻልሽውን ክፋት ሁሉ
ታደርጊያለሽ::"

## ከዳተኛዋ እስራኤል

[6]እግዚአብሔር በንጉሥ ኢዮስያስ ዘመን እንዲህ አለኝ፤ "ከዳተኛዪቱ እስራኤል ያደ ረገችውን አየህን? ከፍ ወዳለው ኰረብታ ሁሉ ወጥታ፣ ወደ ለመለመው ዛፍ ሥር ሁሉ ሄዳ በዚያ አመነዘረች:: [7]ይህን ሁሉ ካደረገች በኋላ፣ ወደ እኔ ትመለሳለች ብዬ ነበር፤ ሆኖም አልተመለሰችም፤ ከሐዲዋ እኅቷ ይሁዳም ይህን አየች:: [8]ለከዳተ ኛዪቱ እስራኤል ስለ ምንዝርናዋ ሁሉ

2፥33 ቍ 23
2፥34 ዘፀ 22፥2፤ 2ነገ21፥16፤ምሳ6፥17
2፥35 2ሳሙ12፥13፤ ምሳ30፥12፤ኢሳ66፥16፤ኤር25፥31፤39፥7፤ 45፥5፤ሕዝ17፥20፤ 20፥35፥ኢል3፥2፤ 1ዮሐ1፥8:10
2፥36 መዝ108፥12፤ ኢሳ30፥2: 3:7፤ኤር31፥22፤37፥7
2፥37 2ሳሙ13፥19፤ ኤር37፥7
3፥1 ዘፍ3፥17፤ዘዳ 24፥1-4፤2ነገ16፥7፤ ኢሳ1፥21፤ኤር2፥20: 25፤4፥30፤ሰቆ1፥2፤ ሕዝ16፥26:29፤ሆሴ 2፥5:7:12፤3፥1
3፥2 ቍ9:21፤ዘፍ 38፥14፤ዘኍ15፥39፤ ኢሳ1፥21፤ሕዝ16፥25
3፥3 ዘሌ26፥19፤ ዘዳ11፥14፤ኤር5፥25፤ 6፥15፤14፥4፤ሕዝ3፥7፤ 16፥30፤8፥12፤ኢል 1፥10፤አሞ4፥7፤ሶፎ 2፥1፤3፥5
3፥4 ቍ19፤ዘዳ32፥6፤መዝ89፥26፤ኢሳ 63፥16፤64፥8፤ኤር 31፥9፤2፥2
3፥5 መዝ103፥9፤ ኢሳ54፥9
3፥6 ቍ12:22፤ ዘሌ17፥7፤ ዘዳ12፥2፤ 1ዜና3፥14፤ኢሳ 24፥16፤ኤር2፥20፤ 17፥2፤31፥22፤49፥4፤ ሕዝ20፥28፤ሆሴ4፥13
3፥7 ሕዝ16፥46፤ 23፥2:11፤አሞ4፥8

3፥21፤ 13፥25፤ ኢሳ17፥10፤ ሕዝ22፥12፤ 23፥35፤ ሆሴ8፥14 ይመ:: እስራኤል ዘወትር አምላኳን እግዚአብሔርንና ያደረገላትን ሁሉ "ማስታወስ" ነበረባት (ዘዳ7፥18፤ 8፥18)፤ ስለዚህም በእርሱ ብቻ በመታመን እርሱን ማምለክ ነበረባት፤ ነገር ግን ብዙ ጊዜ "ረስታዋለች"፤ ከልቧም አውጥታ ጥላዋለች (መሳ2፥10፤ ሆሴ 2፥13 ይመ)::

2፥33 *በፍትወት፤* የአሕዛብን አማልክት ማምለክን የሚመ ለክት ነው (የቍ20 ማብ ይመ)::

*2፥34፤* አሞ2፥6-8፤ 4፥1፤ 5፥11-12 ይመ:: *በስርቆት ያልያ ዝሻቸው፤* ዘፀ22፥2 እና ማብ ይመ::

2፥36 *አሦር እንዳዋረደሽ ግብፅም እንዲሁ ...፤* ቍ15-18 እና ማብ ይመ:: እዚህ ላይ የአካዝን ዘመን (2ዜና28፥21 ይመ)፣ ምናልባት የሴዴቅያስንም ዘመን (37፥7 ይመ) ሊያመለክት ይችላል::

2፥37 *እጆችሽን በራስሽ ላይ አድርገሽ፤* የጥንት ቅርጻ ቅርጽ ሥራዎች፣ ምርኮኞች የእጃቸውን አንጓ ከራሳቸው በላይ አንድ ላይ ተጠፍሮ ያሳያሉ:: *የታመንሽባቸው፤* ግብፅና አሦር ናቸው::

3፥1 *ሰው ... አትረክስምን?* ከዘዳ24፥1-4 ጋር ያነጻጽሩ:: ከተፋቱ በኋላ ዳግመኛ ተጋብቶ አብሮ መኖር የሚያረክሰው ተጋቢዎቹን ብቻ ሳይሆን፣ የሚኖሩባትን ምድር ጭምር ነው (ከቍ2፤ ከዘሌ18፥25-28 ጋር ያነጻጽሩ):: *አመንዝረሻል፤* የ2፥20 ማብ ይመ:: *ከብዙ፤* የ2፥28 ማብ ይመ:: *ወደ እኔ መመለስ፤* በእኔ ላይ ስላደረስሽው በደል ንስሓ ግቢ ማለት ነው (ቍ12-14: 22፤ 4፥1 ይመ)::

3፥2 *ጭር ያሉትን ኰረብቶች፤* የአሕዛብ አማልክት ምክር የሚጠየቁበትና የሚመለኩበት ስፍራ ማለት ነው (ቍ21፤ 12፥12፤ ዘኍ23፥3 ይመ):: *በርኵሰት ያልተጋደምሽበት፤* ከዘዳ 28፥30 ጋር ያነጻጽሩ:: *በየመንገዱ ዳር ተቀምጠሽ፤* ዘፍ38፥14 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም ምሳ7፥10:12 ይመ:: መንፈሳዊ አመንዝራነት ከዚህ አገላለጽ ጋር ተያይዞ ይበልጥ የተብራራው በሕዝ16፥25 ላይ ነው:: *ዘላን ዐረብ፤* መንገደኛን ለመዝረፍ አድፍጦ የተቀመጠ ነው (ሉቃ10፥30 ይመ):: *ምድሪቱን አረከ ስሽ፤* ቍ9 ይመ::

3፥3 *ካፊያ ተከለከለ፤* 14፥1-6፤ አሞ4፥7-8 ይመ:: ይህ፣ እግዚአብሔር ለሕዝቡ በሆሴ2፥21፤ 6፥3 የሰጠው የቸርነት መልስ ተቃራኒ ነው:: *ኋለኛው ዝናብም፤* የዘዳ11፥14 ማብ ይመ:: *የጋለ ሞታ ገጽታ፤* ምሳ7፥13 ይመ::

3፥4 *አባቴ፤* ቍ19 ይመ፤ ከ2፥27 ጋር አገናዝበው፣ ማብ ይመ:: ከአዲስ ኪዳን ጋር ሲነጻጸር፣ "አባቴ" የሚለው ቃል በብሉይ ውስጥ ለእግዚአብሔር መጠሪያነት ውሎ የሚገኘው እጅግ አነስተኛ በሆነ ቍጥር ነው፤ ሆኖም በሰዎች መጠሪያ ስሞች ውስጥ ተደራቢ ሆኖ ይገኛል (ለምሳሌ:- አቢናዳብ፣ አቢ ራም፣ በሚሉት ስሞች ውስጥ 'አቢ' የሚለው ተቀጣይ "እግዚ አብሔር አባተ" የሚል ትርጒም ይይዛል):: *ወዳጄ፤* ቅርበት መኖሩን የሚያሳይ ነው (መዝ55፥13፤ ምሳ16፥28፤ 17፥9፤ ሚክ 7፥7 ይመ)፤ ምናልባትም ራሷን እንደ እግዚአብሔር ታማኝ አድ ርጋ በመቍጠር ሊሆን ይችላል (ከምሳ 2፥17 ጋር ያነጻጽሩ):: *የልጅነት፤* የ2፥2 ማብ ይመ::

3፥5 *ቍጣህስ ለዘላለም ነውን?* የእግዚአብሔር ሕዝብ ንስሐ ከገባ እንደዚያ አይሆንም (ቍ12-13)::

*3፥6-6፥30፤* ይሁዳ ታማኝ ሆና አለመገኘቷ (3፥6-5፥31)፣ በመጨረሻ ላይ ባቢሎናውያን የእግዚአብሔር የመቅጫ ዱላ ሆነው እንዲመጡ አድርጎአል(ምዕ6)::

3፥6 *በንጉሥ ኢዮስያስ፤* የ1፥2 ማብ ይመ፤ ከ640-609 ዓ.ቅ.ክ. ነገሠ:: *ከዳተኛዪቱ እስራኤል፤* በ722-721ዓ.ቅ.ክ. የጠ ፋውን የሰሜኑን መንግሥት ይመለከታል (ቍ8:11-12 ይመ):: *ከፍ ወዳለው ኰረብታ ... ወደ ለመለመው ዛፍ ሥር ሁሉ ...፣ በዚያ አመነዘረች፤* የ2፥20 ማብ ይመ::

3፥7 *ከሐዲዋ እኅቷ ይሁዳ፤* የደቡቡ መንግሥት ነው (ቍ8:10-11 ይመ)፤ ሰማርያ (የእስራኤል ዋና ከተማ) እንዲሁም ኢየሩሳሌም (የይሁዳ ዋና ከተማ) በሕዝ23 ላይ በተመሳሳይ ሁኔታ አመንዝራ እኅትማማቾች እንደ ሆኑ ተደርገው ተነጻጽረዋል:: *ይህን፤* የእስራኤልን አመንዝራነት ማለት ነው::

የፍች ወረቀቷን ሰጥቼ አባረርኋት:: ከሓዲዋ እኅቷ ይሁዳም ይህን አይታ እንዳልፈራች አየሁ፤ ወጥታም አመነዘረች:: [9]በቅሌቷም ምድሪቱን አረከሰች፤ ከድንጋይና ከግንድ ጋር አመነዘረች፤ [10]ይህም ሁሉ ሆኖ ከሓዲዋ እኅቷ ይሁዳ ወደ እኔ የተመለሰችው በማስመሰል እንጂ በሙሉ ልቧ አልነበረም" ይላል እግዚአብሔር::

[11]እግዚአብሔር እንዲህ አለኝ፤ "ከከሓዲዋ ይሁዳ ይልቅ ከዳተኛዪቱ እስራኤል ጻድቅ ሆና ተገኘች:: [12]ሂድና ይህን መልእክት ወደ ሰሜን እንዲህ ብለህ ተናገር፤

" 'ከዳተኛዪቱ እስራኤል ሆይ፤ ተመለሽ'
ይላል እግዚአብሔር፤
'እኔ መሓሪ ስለ ሆንሁ፣
ከእንግዲህ በቍጣ ዐይን አላይሽም'
ይላል እግዚአብሔር::
'ለዘላለም አልቈጣም::
[13]በደልሽን ብቻ እወቂ፤ በእግዚአብሔር ላይ
በማመፅሽ፣
ክብርሽንም ለእንግዶች አማልክት፣
በየለምለሙ ዛፍ ሥር አሳልፈሽ
በመስጠት፣
ለእኔ ባለመታዘዝሽ፣
በደለኛ መሆንሽን ይህን አንድ ነገር
ብቻ እመኚ' "
ይላል እግዚአብሔር::

[14]"ከዳተኛ ልጆች ሆይ፤ እኔ ባለቤታችሁ ነኝና ተመለሱ" ይላል እግዚአብሔር፤ "ከአንድ ከተማ አንድ፣ ከአንድ ነገድ ሁለት

3፥8 ዘዳ24፥27፤ኢር 11፥10፥24፥11፤ሕዝ 16፥47፥23፥11
3፥9 ቍ2፤ዘሌ17፥7 ፤ኢሳ1፥21፥57፥6፤ ኤር2፥27
3፥10 2ነገ17፥19፤ ኢሳ31፥6፤ኤር12፥2 ፤ሕዝ33፥31፤አሞ4፥9 ፤ሐጌ2፥17
3፥11 ቍ7፤ኤር 2፥19፤ሕዝ16፥52፤ 23፥11
3፥12 ቍ6፥14 ዘዳ4፥30፤ 1ነገ8፥26፤ 2ነገ17፥3-6፤መዝ6፥2 ፤103፥9፤ኢሳ54፥9፤ ኤር31፥21፥22፤ሕዝ 14፥6፥33፥11፤ሆሴ 14፥1
3፥13 ቍ25፤ ዘዳ12፥2፥30፥1-3፤ ኤር2፥25፥14፥20፤ 22፥21፥1ዮሐ1፥9
3፥14 ቍ12፤ኢዮ 22፥23፤ኢሳ54፥5፤ ኤር 4፥1
3፥15 ኢሳ31፥4፤ ሐሥ13፥22
3፥16 ዘኍ3፥31፤ 1ዜና 15፥25፤ኢሳ 65፥17
3፥17 መዝ22፥23፤ 47፥8፤ 81፥12፤ኢሳ 2፥3፤ኤር7፥24፥9፥14፤ 11፥8፥13፥10፥11፥16፤ 12፥17፥12፥18፥12፤ 33፥9፥16፤ሕዝ1፥26፤ 43፥7፥48፥35፤ሚክ 4፥1
3፥18 ዘዳ31፥7፤ኢሳ 11፥13፥14፥1፤ኤር 16፥15፥30፥3፥31፥8፤

መርጬችሁ ወደ ጽዮን አመጣችኋለሁ:: [15]እንደ ልቤም የሆኑ፣ በዕውቀትና በማስተዋል የሚመሯችሁን እረኞች እሰጣችኋለሁ:: [16]ቍጥራችሁ በምድሪቱ እጅግ በሚበዛበት ጊዜም ይላል እግዚአብሔር፤ "በዚያን ዘመን፣ 'የእግዚአብሔር የኪዳኑ ታቦት' ብለው ከእንግዲህ አይጠሩም፤ ትዝ አይላቸውም፤ አያስታውሱትምም፤ አይጠፋም፤ ሌላም አይሠራም:: [17]በዚያ ጊዜ ኢየሩሳሌምን፣ 'የእግዚአብሔር ዙፋን' ብለው ይጠሯታል፤ መንግሥታትም ሁሉ የእግዚአብሔርን ስም ለማክበር በኢየሩሳሌም ይሰበሰባሉ፤ የክፉ ልባቸውንም እልኸኝነት ከእንግዲህ አይከተሉም:: [18]በዚያ ዘመን የይሁዳ ቤትና የእስራኤል ቤት በአንድነት ሆነው ከሰሜን ምድር ለአባቶቻቸው ርስት አድርጌ ወደ ሰጠኋቸው ምድር ይመጣሉ::

[19]"እኔም፣
" 'የተመረጠችውን ምድር፣
የትኛውም ሕዝብ ያላገኘውን የተዋበች
ርስት ልሰጥሽ፣
እንደ ወንዶች ልጆቼ ምንኛ በደስታ
ልቈጥርሽ" አልሁ፤
'አባቴ' ብለሽ የምትጠሪኝ፣
እኔንም ከመከተል ዘወር የማትይ
መስሎኝ ነበር::
[20]የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ለባሏ ታማኝ
እንዳልሆነች ሚስት፣
ስታታልሉኝ ኖራችኋል፤"
ይላል እግዚአብሔር::

3፥8 *የፍች ወረቀቷን፤* ቍ1 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዘዳ24፥1-14፤ ኢሳ50፥1 እና ማብ ይመ:: *አባረርኋት፤* በ721 ዓ.ቅ.ክ ወደ ምርኮኝነት ማለት ነው:: *ይሁዳም ... እንዳልፈራች፤* የእስራኤልን አሳዛኝ መከራ አይታ ለመማር አልቻለችም፤ ለመማርም አልፈለገችም::

3፥9 *ከድንጋይና ከግንድ ጋር አመነዘረች፤* የአረማውያንን ባዕዳን አማልክት አመለከች (2፥27 ይመ)::

3፥10 *በማስመሰል፤* ንጉሡ ኢዮስያስ ሳከናወነው የተሐድሶ ተግባር (የ1፥2 ማብ ይመ) ይሁዳ ያሳየችው ሁኔታ ከአንገት በላይና የግብዝነት ነበር::

3፥11 *ከ ... ይሁዳ ይልቅ ... እስራኤል ጻድቅ ሆና ተገኘች፤* የቍ8 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ሕዝ16፥51-52፤ 23፥11 ይመ::

3፥12 *ሂድና ... ተናገር፤* 2፥2 ይመ:: *ሰሜን፤* ብዙ እስራኤላውያን በምርኮ የተወሰዱበት፣ ሰሜናዊው የአሦር መንግሥት አካል ማለት ነው:: *ተመለሺ፤* ንስሐ ግቢ ማለት ነው (ቍ13):: *መሓሪ፤* በሌላ ቦታ የእግዚአብሔርን ባሕርይ ለመግለጽ (መዝ 145፥13፥17)፣ ይህ ቃል በዕብራይስጥ "እፍቃሪ" የሚለውን ትርጕም ይዞአል:: *ለዘላለም አልቈጣም፤* የቍ5 ማብ ይመ::

3፥13 *ክብርሽንም ... አሳልፈሽ በመስጠት፤* ሕዝ 16፥15፡33-34 ይመ:: ለእንግዶች አማልክት፤ የ2፥25 ማብ ይመ:: *በየለምለሙ ዛፍ ሥር፤* የ2፥20 ማብ ይመ::

3፥14 *ባለቤታችሁ፤* 31፥32፤ ሆሴ2፥16-17 ይመ:: ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል 'ባል' ተብሎ ሊተረጐም ይችላል፤ የእግዚአብሔር ሕዝብ የቃል ኪዳን ባላቸውን እግዚአብሔርን ትተው "በአሊምን" ተከተሉ (2፥23፤ የመሳ2፥11 ማብ ይመ):: *ከአንድ ... ሁለት፤* ከሕዝቡ ቅሬታ ወደ አገሩ የሚመለስ ይኖራል (የኢሳ10፥20-22 ማብ ይመ):: *ጽዮን፤* ኢየሩሳሌምን ነው::

*3፥15፤* 23፥4 ይመ:: *እረኞች፤* አስተዳዳሪዎችን ይመለከታል (የ2፥8 ማብ ይመ):: *እንደ ልቤም የሆኑ፤* እንደ ዳዊት ያሉ ናቸው (1ሳሙ13፥14 ይመ፤ በተጨማሪም ሕዝ34፥23፤ ሆሴ3፥5 ይመ)::

3፥16 *በዚያ ዘመን፤* መሲሑ በምድር ላይ በሚገለጥበት ዘመን ነው (ቍ18፤ 31፥29 ይመ):: *ቍጥራችሁ ... በሚበዛበት ጊዜም፤* 23፥3፤ ሕዝ36፥11 ይመ:: የዚህን ሐረግ ሰፋ ያለውን የዕብራይስጥ ትርጕም ለመረዳት የዘፍ1፥28 ማብ ይመ:: *ሌላም አይሠራም፤* የእግዚአብሔርን ግርማዊ ሕልውና በሰዎች መካከል መገኘት የሚያመለክተው (በ1ሳሙ4፥3 ይመ) የኪዳኑ ታቦት፤ መሲሑ በሚመጣበት ዘመን አስፈላጊነቱ ያከትማል::

3፥17 *ዙፋን፤* እግዚአብሔር "በኪሩቤል መካከል" በኪዳኑ ታቦት ላይ ይቀመጥ ነበር (1ሳሙ4፥4 እና ማብ ይመ)፤ ሆኖም ኢየሩሳሌም ራሷ አንድ ቀን መቀመጫ ዙፋኑ ትሆናለች:: *መንግሥታትም ሁሉ ... ይሰበሰባሉ፤* ዘካ2፥11 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ2፥2-4 ማብ ይመ:: *የክፉ ልባቸውንም እልከኝነት ... አይከተሉም፤* የእስራኤልን አለመታዘዝና ብዙውን ጊዜ ወደ ጣዖት አምልኮ ማዘንበል ለማመልከት የገባ፣ የተለመደ ተደጋጋሚ ሐረግ ነው (9፥14፥11፥8፤ 13፥10፥16፥12፤ 18፥12፤ 23፥17 ይመ)::

3፥18 *የይሁዳ ቤትና የእስራኤል ቤት በአንድነት ሆነው፤* የተከፋፈለው የእግዚአብሔር ሕዝብ በመሲሑ ዘመን እንደ ገና ተመልሶ አንድ ይሆናል (ለምሳሌ:-ኢሳ11፥12፤ ሕዝ37፥15-23፤ ሆሴ1፥11 ይመ):: *ከሰሜን ምድር፤* በምርኮ የቆዩበት አገር ማለት ነው (የቍ12 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 31፥8 ይመ):: *ርስት አድርጌ ወደ ሰጠኋቸው ምድር፤* የ2፥7 ማብ ይመ::

3፥19 *ልጆቼ፤* እስራኤል የእግዚአብሔር የበኵር ልጅ ነበረች (ዘፀ4፥22 ይመ፤ ከሆሴ11፥1 ጋር ያነጻጽሩ):: *የተመረጠችውን ምድር፤* ይህ በዕብራይስጥ በመዝ106፥24 እና በዘካ7፥14 "የተወደደችው ምድር" ተብሎ ተተርጕሞአል:: *የተዋበች ርስት፤* ይሁዳና ኢየሩሳሌም፣ ሕዝቡም ራሳቸው በእግዚአብሔር ፊት እንደ ውብ ነገር ይቈጠሩ ነበር (6፥2፤ 11፥16 ተመ):: *አባቴ፤* የቍ4 ማብ ይመ::

*3፥20፤* በሆሴ ም1-3 ላይ የቀረበው ትረካ፣ በዚህ ቍጥር ላይ እጥር ምጥን ብሎ ቀርቦአል::

[21]እግዚአብሔር አምላካቸውን በመርሳት፣
መንገዳቸውን አጣመዋልና፣
የእስራኤል ሕዝብ ጩኸት፣
አሳዛኝ ልቅሶ ባድማ ከሆኑት
ኰረብታዎች ተሰማ።

[22]"እናንተ ከዳተኞች ልጆች ተመለሱ፤
ከዳተኝነታችሁን እፈውሳለሁ።"
"አንተ እግዚአብሔር አምላካችን ነህና፤
አዎን፤ ወደ አንተ እንመጣለን።
[23]በእርግጥ በኰረብቶች ላይ፣
እንዲሁም በተራሮች ላይ፣ ሆ! ብለን
መውጣታችን መታለል ነው፤
በእርግጥ የእስራኤል መዳን፣
በአምላካችን በእግዚአብሔር ነው።
[24]ከለጋ ዕድሜአችን ጀምሮ፣
የአባቶቻችንን የድካም ፍሬዎች፣
በጎቻቸውንና ከብቶቻቸውን፣
ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን፣
ነውረኛ ጣዖቶች በሏቸው።
[25]እንግዲህ ዕፍረታችንን ተከናንበን እንተኛ፤
ውርደታችንም ይሸፍነን፤
እኛም አባቶቻችንም፣
እግዚአብሔር አምላካችንን በድለናልና፤
ከልጅነታችን ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ፣
አምላካችንን እግዚአብሔርን
አልታዘዝንም።"

4 "እስራኤል ሆይ፤ ብትመለስ፣
ወደ እኔ ብትመለስ፤"
ይላል እግዚአብሔር፤
"አስጸያፊ ነገሮችህን ከፊቴ ብታስወግድ፣
ባትናወጥ ብትቆምም፣
[2]በእውነት፣ በቅንነትና በጽድቅ፣
'ሕያው እግዚአብሔርን!' ብለህ
ብትምል፣
አሕዛብ በእርሱ ይባረካሉ፤
በእርሱም ይከበራሉ።"

[3]እግዚአብሔር ለይሁዳና ለኢየሩሳሌም ሰዎች
እንዲህ ያላል፤
"ዕዳሪውን መሬት ዕረሱ፤
በእሾህም መካከል አትዝሩ።
[4]እናንተ የይሁዳ ሰዎች፣ የኢየሩሳሌምም
ነዋሪዎች፤
ለእግዚአብሔር ተገረዙ፤
የልባችሁንም ሸለፈት አስወግዱ፤
አለዚያ ስለ ሠራችሁት ክፋት፣
ቍጣዬ እንደ እሳት ይንበለበላል፤
ሊገታውም የሚችል የለም።

### ጥፋት ከሰሜን መምጣቱ

[5]"'በምድሪቱ ሁሉ መለከትን ንፉ'
ብላችሁ፤
በይሁዳ ተናገሩ፣ በኢየሩሳሌም ዐውጁ፤
ጮኹ፤ እንዲህም በሉ፤
'በአንድነት ተሰብሰቡ፤
ወደ ተመሸጉት ከተሞች እንሽሽ!'
[6]ወደ ጽዮን ለመግባት ሰንደቅ ዐላማ
አንሡ፤
ቶሎ ሽሽታችሁ አምልጡ፤
ከሰሜን መቅሠፍትን፣
ታላቅ ጥፋትን አመጣለሁና።"
[7]አንበሳ ከደኑ ወጥቶአል፤
ሕዝብንም የሚያጠፋ ተሰማርቶአል፤
ምድርሽን ባዶ ሊያደርግ፣
ከስፍራው ወጥቶአል።

50፥4፤ሕዝ11፥17፤ 37፥19፡22፤አሞ9፥15
3፥19 ቍ4፤ዘፀ4፥22፤ዘዳ8፥7፤2ሳሙ7፥14፤መዝ106፥24፤ ሕዝ 20፥6
3፥20 ኢሳ 24፥16
3፥21 ቍ2፤ኢሳ 57፥11፤ኤር31፥18
3፥22 ቍ12፤ኢዮ 22፥23፤ኢሳ30፥26፤ 57፥18፤ኤር2፥19፤ 33፥6፤ ሆሴ 6፥1
3፥23 መዝ3፥8፤ኤር 2፥20፤ 17፥14
3፥24 ኤር11፥13፤ ሆሴ9፥10
3፥25 ቍ13፤ መሳ10፥10፤1ነገ 8፥47፤ዕዝ9፥6፤መዝ 25፥7፤ኤር14፥20፤ 22፥21፤31፥19፤ሕዝ 2፥3፤ ዳን 9፥7
4፥1 ዘዳ4፥30፤ 2ነገ 17፥13፤21፥4፤ኤር 16፥18፤35፥15፤ሕዝ 8፥5 ሆሴ 12፥6
4፥2 ዘፍ12፥2፤ዘኍ 14፥21፤ዘዳ10፥20፤ ኢሳ19፥18፤ 65፥16፤ ኤር5፥2፤9፥24፤12፥ 16፤44፥26፤ሆሴ4፥15 ፤ገላ3፥8
4፥3 ሆሴ10፥12፤ ማር4፥18
4፥4 ዘፀ 32፥22፤ ዘሌ26፥41፤ኢዮ41፥ 21፤ኢሳ1፥31፤አሞ 5፥6፤ሶፎ1፥18፤2፥2
4፥5 ቍ21፤ዘኍ10፥ 2፡7፤ኢሱ10፥20፤ኢዮ 39፥24፤ኤር5፥20፤ 11፥2፡6
4፥6 ቍ21፤መዝ 74፥4፤ኢሳ11፥10፤ 14፥31፤31፥9፤ኤር

3፥21 *ባድማ ከሆኑት ኰረብታዎች፤* የቍ2 ማብ ይመ። *አሳዛኝ ልቅሶ፤* የንስሐ ጩኸት ሲሆን፣ በቍ22ለ-25 ላይ በቃላት ተገልጾአል። *በመርሳት፤* የ2፥32 ማብ ይመ።

*3፥22፤* ቍ14 ይመ። *ከዳተኞች ... ተመለሱ፤ ከዳተኝነታችሁን፤* እነዚህ ሦስት ቃላት በዕብራይስጡ ከአንድ ሥርዎ ቃል የተገኙ ናቸው፤ በመሆኑም በዚያ ቋንቋ ሲነበቡ ተመሳሳይ ድምፅ አላቸው። *እፈውሳለሁ፤* 30፥17፤ 33፥6፤ ሆሴ6፥1፤ 14፥1፡4 ይመ። አዎን፤ ሕዝቡ ንስሐ መግባት መጀመሩን ያመለክታል።

3፥23 *ሆ ብለን መውጣታችን፤* ለምሳሌ፦ 1ነገ18፥25-29 ይመ። *መዳን ... በእግዚአብሔር ነው፤* ዘፍ49፥18፤ መዝ3፥8፤ ዮና2፥9 እና ማብ ይመ።

3፥24 *ከለጋ ዕድሜአችን፤* ከእስራኤል ሕዝብ አንጻር ሲታይ ዘመነ መሳፍንትን የሚያመለክት ነው። *ነውረኛ ጣዖቶች፤* የ2፥26፤ 11፥13 ማብ ይመ። *ፍሬዎች ... በሏቸው፤* ባዕድ አምልኮ ገንዘብ ከማግኘትም ሆነ ከመንፈሳዊ አንጻር ሲታይ እርባና የለሽ ነው። *ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸው፤* ብዙውን ጊዜ ለአረማውያን ባዕዳን አማልክት መሥዋዕት ሆነው ይቀርቡ ነበር (የ7፥31 ማብ ይመ)።

3፥25 *ዕፍረታችንን፤* ለዚህ የሚውለው የዕብራይስጡ ተመሳሳይ ቃል በቍ24 ላይ "ነውረኛ ጣዖቶች" ተብሎ ተተርጕሞአል።

4፥1 *ባትናወጥ፤* ለዚህ ቃል የገባው የዕብራይስጡ አቻ ትርጕም፣ መቅበዝበዝን ያመለክታል፤ ይኸውም በዘፍ 4፥12፡14 እንደ ተጠቀሰው ዐይነት ማለት ነው (የዘፍ4፡16 ማብ ይመ)።

4፥2 *በእውነት፣ በቅንነትና በጽድቅ፤* አጎልማሽ ቃላት በተከታታይ መደርደራቸው፣ ከአንገት በላይ ያልሆነ፣ ነገር ግን ከልብ የመነጨ ንስሓ እንደሚያስፈልግ አበክሮ ለመግለጽ ነው። *ሕያው እግዚአብሔርን!* የዘፍ42፥15 ማብ ይመ። *አሕዛብ በእርሱ ይባረካሉ፤* እግዚአብሔር ለአብራም ከገባቸው ዐበይት ቃል ኪዳኖች ውስጥ ሰባተኛውን የተስፋ ቃል የሚያንጸባርቅ አባባል ነው (ዘፍ12፥2-3 እና ማብ ይመ)። ለሕዝቦች መባረክ፣ ለእስራኤል ንስሓ መግባት ተፈላጊ እርምጃ ነው።

4፥3 *ዕዳሪውን መሬት ዕረሱ፤* ምናልባት ከሆሴ 10፥12 የተጠቀሰ ሊሆን ይችላል። *በእሾህም መካከል አትዝሩ፤* ማቴ 13፥7፡22 ይመ። ለእግዚአብሔር ሙሉ በሙሉ መገዛት አስፈላጊ እንደ ሆነ ሁሉ (ሕዝ18፥31 ይመ)፣ እግዚአብሔር ለሚያቀርብልን ጥሪም ልብን ክፍት አድርጎ መቅረብ ያስፈልጋል።

4፥4 *የልባችሁንም ሸለፈት አስወግዱ፤* ልባችሁን ቀድሱ (6፥10፤ 9፥26፤ ዘፍ17፥10 እና ማብ፤ ዘዳ10፥16፤ 30፥6 ይመ)። *ስለ ሠራችሁት ክፋት፤* ምናልባት ከዘዳ28፥20 የተጠቀሰ ሊሆን ይችላል። *ቍጣዬ ... ይንበለበላል፤ ሊገታውም የሚችል የለም፤* 21፥12፤ ኢሳ1፥31፤ አሞ5፥6 ይመ።

*4፥5-31፤* ንስሓ ለመግባት ፈቃደኛ ባልሆኑት የእግዚአብሔር ሕዝብ ላይ ወራሪ ኀይል ከሰሜን መጥቶ የእግዚአብሔርን ፍርድ ያደርስባቸዋል(ም6 ይመ)።

4፥5 *መለከትን ንፉ፤* ሊመጣ ካለው ከባድ መከራ ለማስጠንቀቅ ነው (6፥1 ይመ፤ የኢል2፥1 ማብ በተጨማሪ ይመ)። *ወደ ተመሸጉት ከተሞች እንሽሽ!* ቍ6 ይመ። በገጠር የሚኖሩ ሰዎች ወራሪ ሰራዊት በምርኮ ይዞአቸው እንዳይሄድ፣ በአቅራቢያቸው ወደሚገኝ ቅጥር ወዳለው ከተማ በመሸሽና በመጠለል ይተርፉሉ (5፥17፤ 8፥14፤ 34፥7፤ 48፥18 ይመ)።

*4፥6፤* 6፥1 ይመ። *ሰንደቅ ዐላማ አንሡ፤* የኢሳ 5፥26 ማብ ይመ። *ከሰሜን መቅሠፍትን፤* ባቢሎናውያንን ያመለክታል (1፥14 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ 41፥25 ማብ ይመ)። *ታላቅ ጥፋትን፤* 6፥1 ይመ፤ ከ48፥3፤ 50፥22፤ 51፥54 ጋር ያነጻጽሩ።

4፥7 *አንበሳ፤* የባቢሎን ምልክት ነው (የ2፥15 ማብ ይመ)። *የሚያጠፋ፤* ብዙውን ጊዜ ባቢሎንን የሚያመለክት ነው (6፥26፤ 15፥8፤ 48፥ 8፡32)፣ ይሁን እንጂ በ51፥1፡56 ላይ ፋርስንና ግብረ አበሮቿን ያመለክታል (51፥48፡53 ይመ)። *ከተሞ*

ከተሞችሽ ፈራርሰው ይወድቃሉ፤
ያለ ነዋሪም ይቀራሉ።
[8]ስለዚህ ማቅ ልበሱ፤
እዘኑ፤ ዋይ በሉ፤
የእግዚአብሔር አስፈሪ ቍጣ፣
ከእኛ አልተመለሰምና።

[9]"በዚያ ቀን" ይላል እግዚአብሔር፣
"ንጉሡና ሹማምንቱ ወኔ ይከዳቸዋል፤
ካህናቱ ድንጋጤ ይውጣቸዋል፤
ነቢያቱም ብርክ ይይዛቸዋል።"

[10]እኔም፣ "ጌታ እግዚአብሔር ሆይ፤ ሰይፍ አንገታቸው ላይ ተቃጥቶ ሳለ፣ 'ሰላም ይሆንላችኋል' ብለህ ይህን ሕዝብና ኢየሩሳሌምን ለምን እጅግ አታለልህ?" አልሁ።

[11]በዚያ ጊዜ፣ ለዚህ ሕዝብና ለኢየሩሳሌም እንዲህ ተብሎ ይነገራል፤ "ለማበጠር ወይም ለማጥራት ሳይሆን፣ ከዚያ የበረታ የሚጠብስ ደረቅ ነፋስ በምድረ በዳ ካሉት ባድማ ኰረብቶች ወደ ወገኔ ሴት ልጅ [12]በእኔ ትእዛዝ ይነፍሳል፤+ እንግዲህ ፍርዴን በእነርሱ ላይ እናገራለሁ።"

[13]እነሆ፤ እንደ ደመና ይንሰራፋል፤
ሠረገሎቹ እንደ ዐውሎ ነፋስ ይመጣሉ፤
ፈረሶቹም ከንስር ይፈጥናሉ፤
መጥፋታችን ነውና ወዮልን!
[14]ኢየሩሳሌም ሆይ፤ እንድትድኚ ከልብሽ
ክፋት ታጠቢ፤
እስከ መቼ ክፉ ሐሳብ በውስጥሽ
ይኖራል?
[15]ድምፅ ከዳን ይሰማልና፤
ከኤፍሬም ተራሮችም ጥፋትን ያውጃል።
[16]"ይህን ለሕዝቦች አሳውቁ፤
ለኢየሩሳሌምም እንዲህ ብላችሁ በይፋ
ንገሩ፤
'ከበው የሚያስጨንቁ ከሩቅ አገር
ይመጣሉ፤
በይሁዳ ከተሞችም ላይ ይደነፋሉ፤
[17]ሰብል እንደሚጠብቁ ሰዎች ይከቧታል፤
በእኔ ላይ ዐምፃለችና፤'"
ይላል እግዚአብሔር።
[18]"የገዛ መንገድሽና ተግባርሽ፣
ይህን አምጥቶብሻል፤
ይህም ቅጣትሽ ነው፤
ምንኛ ይመራል!
እንዴትስ ልብ ይሰብራል!"
[19]ወይ አበሳዬ! ወይ አበሳዬ!
ሥቃይ በሥቃይ ላይ ሆነብኝ፤
አወይ፣ የልቤ ጭንቀት!
ልቤ ክፉኛ ይመታል፤
ዝም ማለት አልችልም፤
የመለከትን ድምፅ፣
የጦርነትንም ውካታ ሰምቻለሁና።
[20]ጥፋት በጥፋት ላይ ይመጣል፤
ምድሪቱም በሞላ ባድማ ትሆናለች፤
ድንኳኔ በድንገት፣
መጋረጃዬም በቅጽበት ጠፋ።
[21]እስከ መቼ የጦርነት ዐርማ
እመለከታለሁ?
እስከ መቼስ የመለከት ድምፅ
እሰማለሁ?

11፥11፤18፥11፤ 50፥2፡3
4፥7 ቍ29፤ ዘሌ26፥31፤2ነገ24፥1፤ኢሳ1፥7፤6፥11፤22፥7፤48፥8፤51፥1፡53፤ ኤር2፥15፤6፥26፤ 15፥8፤25፥38፤ሕዝ 12፥20፤1፥31፤25፥7 ሆሴ5፥14፤13፥7፤ናሆ 2፥12፤
4፥8 1ነገ21፥27፤ ኢሳ3፥24፤10፥4፤ኤር 6፥26፤7፥29፤9፥20፤ 30፥24፤ሕዝ7፥18፤ ኢል1፥8፤ አሞ 5፥1
4፥9 1ሳሙ17፥32፤ ኢሳ 29፥9
4፥10 ዘፀ5፥23፤ኢሳ 30፥10፤ኤር6፥14፤8፥11፤14፥13፤23፥17፤ ሕዝ13፥10፤ሚክ3፥5፤ 1ተሰ5፥3፤2ተሰ2፥11
4፥11 ዘፍ41፥6፤ዘሌ 26፥33፤ኢዮ1፥19
4፥12 ኢሳ 64፥6፤ ኤር 1፥16
4፥13 ቍ 20፡27፤ ዘዳ28፥49፤2ሳሙ22፥10፤2ነገ2፥1፤ኢሳ 6፥11፤19፥1፤24፥3፤ 66፥15፤ኤር7፥34፤ 9፥11፡19፤12፥11፤ 25፥11፤44፥6፤ሕዝ 26፥10፤ሚክ2፥4፤ናሆ 2፥4፤ዕን1፥8፤3፥8
4፥14 ሩት3፥3፤መዝ 51፥2፤ 6፥3፤ ኢሳ 45፥22፤ያዕ 4፥8
4፥15 ዘፍ 30፥6፤ ኤር31፥6
4፥16 ቍ19፤ዘዳ28፥49፤ ኤር1፥15፤ ሕዝ 21፥22
4፥17 1ሳሙ12፥15፤ 2ነገ25፥1፡4፤ኤር5፥23
4፥18 መዝ107፥17፤ ኢሳ1፥28፤ኤር5፥25፤2፥17፡19
4፥19 ቍ16፡21፤ዘኍ10፥2፡9፤ኢዮ 4፥2፤6፥10፤14፥22፤37፥1፤39፥24፤ኢሳ22፥4፤ኤር6፥24፤9፥10፤ 10፥19፤20፥9፤23፥9፤49፥2፤ሰቆ1፥20፤ሶፎ1፥16፤
4፥20 ቍ13፤ዘኍ 24፥5፤ዘዳ31፥17፤ኤር10፥20፤ሰቆ2፥4
4፥21 ቍ5፡6፡19፤ዘኍ2፥2፤ ኢሱ6፥20፤ኢሳ18፥3፤ኤር6፥1፤ሆሴ5፥8፤አሞ3፥6፤ሶፎ1፥16

+12 ወይም በእኔ ትእዛዝ የሚመጣው

*ችሽ ... ያለ ነዋሪም ይቀራሉ፤* የ2፥15 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ቍ25፤ 46፥19 ይመ።

4፥8 *ማቅ፤* የዘፍ37፥34 ማብ ይመ። *ቍጣ ... አልተመለሰምና፤* ከ2፥35 ጋር ያገናዝቡ።

4፥9 *በዚያን ቀን፤* የኢሳ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ። *ንጉሡና ሹማምንቱ ... ካህናቱ ... ነቢያቱም፤* የ1፥18 ማብ ይመ።

4፥10 *አታለልህ፤* በቀጥታ ሳይሆን በሐሰት ነቢያት አማካይነት ነው (ለምሳሌ:- 1ነገ22፥20-23 እና የ1ነገ22፥23 ማብ ይመ)። *ሰላም ይሆንላችኋል፤* ይህ የእግዚአብሔር ቃል ሳይሆን፣ ሐሰተኛ ነቢያት ከራሳቸው አፍልቀው የተናገሩት ነው (14፥13፤ 23፥17፤ 6፥13-14፤ 8፥10-11 ይመ)። *አንገታቸው፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል "ነፍስ" ወይም "ሕይወት" ተብሎ ሊተረጐም ይችላል፤ ነገር ግን የቃሉ ትርጕም፣ "ጕሮሮ" ወይም "አንገት" ማለት ነው (ለምሳሌ:- መዝ69፥1 ይመ)።

4፥11 *የሚጠብስ ደረቅ ነፋስ፤* አሸዋና አቧራ አዝሎ የሚጓዝ ሞቃትና ደረቅ ነፋስ ሲሆን፣ ሲሮኮ ወይም ካምሲን በመባል ይታወቃል (መዝ 11፥6፤ ኢሳ 11፥15፤ ዮና 4፥8)። *ለማበጠር፤* የሩት 1፥22 ማብ ይመ።

4፥12 *በእኔ ትእዛዝ ይነፍሳል፤* የእግዚአብሔር ፍርድ በጎውንና ክፉውን አንድ ላይ ጠራርጎ ይወስዳል፤ አማራጭ ትርጕሙን ይመ።

4፥13 *እንደ ደመና ይንሰራፋል፤* ከሕዝ38፥16 ጋር ያነጻጽሩ። *ሠረገሎቹ እንደ ዐውሎ ነፋስ፤* 2ነገ2፥11፤ 6፥17፤ መዝ68፥17፤ ኢሳ66፥15 ይመ። *ፈረሶቹም ከንስር ይፈጥናሉ፤* ባቢሎናውያን (ዕን1፥6) "ከነብር ይልቅ ፈጣኖች" የሆኑና "እንደ ንስር የሚበሩ" ፈረሶች እንደ ነበሯቸው ዕን1፥8 ይመ (በ4፥13 ላይ "ለአሞራ" የገባው የዕብራይስጡ ቃል "ንስር" ተብሎ ተተርጕሞአል፤ ዘዳ28፥49 ይመ)። *መጥፋታችን፤* ቍ20፤ 9፥19፤ 48፥1 ይመ።

4፥14 *ታጠቢ፤* 2፥22 እና ማብ ይመ። *ክፉ ሐሳብ፤* በሌሎች ሰዎች ላይ ማለት ነው (ምሳ 6፥18፤ ኢሳ 59፥7 ይመ)።

4፥15 *ከዳን፤* እጅግ ራቅ ብሎ የሚገኝ ሲሆን፣ ከሰሜኑ የእስራኤል ጠረፍ አጠገብ የሚገኝ አካባቢ ነው (8፥16 ይመ)። *ከኤፍሬም፤* በሰሜን ኢየሩሳሌም ጥቂት ራቅ ብሎ የሚገኝ ቦታ ነው። በነቢዩ ዐይነ ኅሊና ሲታይ ጠላት በአሳፋሪ ሁኔታ ወደ ቅድስቲቱ ከተማ በፍጥነት እየተቃረበ ነው።

4፥16 *ከበው የሚያስጨንቁ* ኢሳ1፥8 ይመ። ሩቅ አገር፤ ባቢሎንን ነው። *ይደነፋሉ፤* ይህን አባባል የሚገልጸው የዕብራይስጡ ተመሳሳይ ቃል በ2፥15 ላይ "አገሡ" ተብሎ ተተርጕሞአል።

4፥17 *ይከቧታል፤* 1፥15 ይመ።

*4፥19-26፤* በቍ22 ላይ እግዚአብሔር የተሰማውን ቅሬታ ገልጦአል፤ ኤርምያስ ሙሉ በሙሉ የራሱን ስሜት የገለጠበት ክፍል ነው። በዚህ ክፍል ኤርምያስም እየተቃረበ የመጣውን የውድ አገሩንና የሕዝቡን ጥፋት በማሰብ፣ አፍ አውጥቶ የልቡን ጭንቀት ሲተነፍስ ይታያል።

*4፥19፤* 10፥19-20 ይመ። *አበሳዬ፤* እዚህ ላይ እንደ ተገለጸው፣ ብዙ ጊዜ ከምጥ ጣር ጋር የተያያዘ ነው (6፥24፤ 49፥24፤ 50፥43 ይመ)። *ልቤ ክፉኛ ይመታል፤* ኢዮ37፥1፤ መዝ 38፥10፤ ዕን 3፥16 ይመ። *የመለከትን ድምፅ፤* የቍ5 ማብ ይመ።

4፥20 *ባድማ ትሆናለች፤* ቍ13፤ 9፥19፤ 48፥1 ይመ። *መጋረጃዬም፤* ዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "የድንኳን መጋረጃ" ማለት ይሆናል (ኢሳ54፥2 ላይ እንደ ተጠቀሰው ማለት ነው)፤ ይህም የሚሠራው ከፍየል ጠጕር በመሆኑ (ዘፀ 26፥7 ይመ)፣ ከብርድና ከዝናብ ሊያድን ይችላል (10፥20 ይመ)።

4፥21 *የጦርነት አርማ ... የመለከት ድምፅ፤* የቍ5-6 ማብ ይመ።

[22]"ሕዝቤ ተላሎች ናቸው፤
እኔን አያውቁኝም::
ማስተዋል የጐደላቸው፣
መረዳትም የማይችሉ ልጆች ናቸው::
ክፋትን ለማድረግ ጥበበኞች፤
መልካም መሥራት ግን የማያውቁ::"

[23]ምድርን ተመለከትሁ፤
እነሆ ቅርጽ የለሽና ባዶ ነበረች፤
ሰማያትንም አየሁ፣
ብርሃናቸው ጠፍቶአል::
[24]ተራሮችን ተመለከትሁ፣
እነሆ ይንቀጠቀጡ ነበር፤
ኰረብቶችም ሁሉ ተናጡ::
[25]አየሁ፤ ሰው አልነበረም፤
የሰማይ ወፎች ሁሉ በረው ጠፍተዋል::
[26]ተመለከትሁ፤ እነሆም፣ ፍሬያማው ምድር
በረሓ ሆነ፤
ከተሞቹ ሁሉ *በእግዚአብሔር* ፊት፣
ከብርቱ ቍጣው የተነሣ ፈራረሱ::

[27]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"ምድር ሁሉ ባድማ ትሆናለች፤
ነገር ግን ፈጽሜ አላጠፋትም::
[28]ስለዚህ ምድር ታለቅሳለች፤
ሰማያትም በላይ ይጨልማሉ፤
ተናግሬአለሁ፤ ሐሳቤን አልለውጥም፤
ወስኛለሁ፤ ወደ ኋላም አልልም::

[29]ከፈረሰኞችና ከቀስተኞች ጩኸት
የተነሣ፣
ከተማ ሁሉ ይሸሻል፤
አንዳንዶች ደን ውስጥ ይገባሉ፤
ሌሎችም ቋጥኝ ላይ ይወጣሉ፤
ከተሞች ሁሉ ባዶ ቀርተዋል፤
የሚኖርባቸውም የለም::

[30]አንቺ ለጥፋት የተዳረግሽ ሆይ፤ ምን
መሆንሽ ነው?
ቀይ ቀሚስ የለበስሽው ለምንድነው?
ለምን በወርቅ አጌጥሽ?
ዐይኖችሽንስ ለምን ተኳልሽ?
እንዲያው በከንቱ ተሽሞንሙነሻል፤
የተወዳጀሻቸው ንቀውሻልና፤
ነፍስሽንም ሊያጠፉ ይፈልጋሉ::

[31]የበኵር ልጇን ለመውለድ እንደምታምጥ፣
በወሊድ እንደምትጨነቅ ሴት ድምፅ
ሰማሁ፤
የጽዮን ሴት ልጅ ትንፋሽ አጥሮአት
ስትጮኽ፣
እጇን ዘርግታ፣
"ወዮልኝ! ተዝለፈለፍሁ፣
በነፍሰ ገዳዮች እጅ ወደቅሁ!" ስትል
ሰማሁ::

**ቅን ሰው አለመገኘቱ**

**5** "በኢየሩሳሌም መንገዶች እስቲ ውጡ፤
ወደ ላይ ወደታችም ውረዱ፤
ዙሪያውን ተመልከቱ ቃኙ፤
በአደባባይዋም ፈልጉ፤
እውነትን የሚሻና በቅንነት የሚሄድ፣
አንድ ሰው እንኳ ብታገኙ፣
እኔ ይህቺን ከተማ እምራታለሁ::
[2]'ሕያው *እግዚአብሔርን!*' ቢሉም፣
የሚምሉት በሐሰት ነው::"

4፥22 መዝ14፥4፤ 36፥3፤53፥2፤10፥8፤ ኢሳ1፥3፤27፥11፤ኤር 2፥8፤5፥21፤6፥6፤ 8፥7፤ 13፥23፤ሆሴ 5፥4፤ 1ቆሮ 14፥20
4፥23 ቍ28፤ ዘፍ 1፥2፤ኢዮ9፥7፤30፥26፤ ኢሳ5፥30፤59፥9፤ሰቆ 3፥2
4፥24 ዘፀ19፥18፤ ኢዮ9፥6
4፥25 ኤር7፥20፤ 9፥10፤12፥4፤ሆሴ4፥3፤ ሶፎ1፥3
4፥26 ዘፍ13፥10፤ ኢሳ6፥11፤ኤር12፥4፡ 13፤23፥10፤25፥38
4፥27 ቍ13፤ዘሌ26 ፥44፤ኤር5፥10፡18፤12 ፥12፤30፥11፤46፥28፤ ሕዝ20፥17፤አሞ 9፥8
4፥28 ቍ8፡23፤ዘኁ 23፥19፤ኤር12፥4፡11፤ 14፥2፤23፥20፤30፥24 ፤ሆሴ4፥3
4፥29 ቍ7፡13፤ዘፀ 33፥22፤1ሳሙ26፥20፤ 2ነገ25፥4፤ኢሳ6፥12፤ ኤር6፥23፤8፥16
4፥30 2ነገ9፥30፤ኢ ዮ19፥14፤መዝ35፥4፤ ኢሳ10፥3-4፤ሰቆ1፥2 ፤ሕዝ16፥11፤23፥9፡ 22፤23፥40
4፥31 ዘፍ3፥16፤ ዘዳ32፥25፤መዝ9፥14፤ ኢሳ42፥14፤1፥15፤ ኤር6፥24፤13፥21፤22 ፥23፤30፥6፤ሰቆ1፥17፤ 2፥21፤ሚክ4፥10
5፥1 ቍ31፤ዘፍ 18፥24፡32፤2ዜና16፥9 ፤መዝ45፥10፤ኤር2፥ 29፤14፥14፤ሕዝ 13፥6፤22፥30
5፥2 ዘሌ19፥12፤ኤር4፥2

*4፥22፤* በዚህ ቦታ የሚናገረው እግዚአብሔር ነው:: ***ተላሎች፤*** ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ግብረ ገብነት የጐደለውን ሰው የሚያመለክት ነው:: ***አያውቁኝም፤*** 2፥8 ይመ:: መሪዎቹም ሆኑ ሕዝቡ እጅግ ክፉ ኀጢአት ፈጽመዋል (ኢሳ 1፥3፤ ሆሴ4፥1 ይመ):: ***ማስተዋል የጐደላቸው፤*** 5፥21፤ 10፥8፡ 14፡21፤ 51፥17 ይመ:: ***ክፋትን ለማድረግ ጥበበኞች፤*** ሚክ7፥3 ይመ::

*4፥23-26፤* በእያንዳንዱ ቍጥር መጀመሪያ ላይ "ተመለ ከትሁ" የሚለው ቃል በሚያስገርም ሁኔታ መደጋገሙ፣ የግጥ ሙን ሐሳብ ከማቈራኘቱም በላይ፣ ባቢሎናውያን መጥተው ውድ አገሩን ካወደሚት በኋላ፣ ነቢዩ ሁኔታውን የተመለከተበትን የራ እይ ጠባይ አበክሮ ያሳያል:: ነባራዊውም ዓለም፣ የተሰጠውን ኵቷና ሞገስ ተገፎ ይታያል::

4፥23 ***ቅርጽ የለሽና ባዶ፤*** ይህ አባባል በዘፍ1፥2 ላይ ብቻ ይገኛል (የዚያን ማብ ይመ):: በሥነ ፍጥረት መጀመሪያ ላይ ይታይ የነበረው ቅጥ አልባነት በኤርምያስ ራእይ ላይ ተመልሶ ታይቶአል:: ***ብርሃናቸው ጠፍቶአል፤*** ከዘፍ1፥3 ጋር ያገናዝቡ::

*4፥24፤* ናሆ1፥5 ይመ::

4፥25 ***ሰው አልነበረም፤*** ይህ ሐረግ በዕብራይስጡ የሚገ ኘው በዘፍ2፥5 ላይ ብቻ ነው፤ በዚያም ክፍል "ሰው አልነበረም" ተብሎ ተተርጒሞአል:: እዚህም ላይ የፍጥረት ሕልውና ወደ አለመኖር ሲለወጥ ይታያል::

4፥26 ***ፍሬያማው ምድር፤*** የ2፥7 ማብ ይመ:: ***ብርቱ ቍጣው፤*** ቍ8፤ ኢሳ13፥13፤ ናሆ1፥6 ይመ::

4፥27 ***ፈጽሜ አላጠፋትም፤*** 5፥10፡18፤ 30፥11፤ 46፥28 ይመ:: ኤርምያስ በቍ23-26 ላይ የጠቀሰውን የእግዚአብሔር ፍርድ፣ በዚህ ቍጥር ላይ የእግዚአብሔር ምሕረት ሲያለዝበው ይታያል::

4፥28 ***ሐሳቤን አልለውጥም፤*** ሕዝቡ ንስሓ ካልገባ ማለት ነው (18፥7-8 ይመ)::

*4፥29፤* ***ከቀስተኞች፤*** ባቢሎን በይሁዳ ላይ በክፋት በመነሣት ቀስተኞችን ብታሰልፍባትም፣ በሌላ ጊዜ ደግሞ ክፋቷ በራሷ ላይ ይመለሳል (50፥29 ይመ):: ***አንዳንዶች ...ይገባሉ፤*** መሳ6፥2፤ 1ሳሙ13፥6፤ ኢሳ2፥19፡21 ይመ:: በተቀጠረ ከተማ ውስጥ የሚኖሩ ሰዎች እንኳ ከሥጋት አያመልጡም:: ***ባዶ ቀርተዋል፤*** ከኢሳ62፥4 ጋር ያገናዝቡ::

4፥30 ***ተኳልሽ፤*** ኵል፣ "አንቲሞኒ" ከሚባለው ንጥረ ነገር የሚሠራ ሲሆን፣ ዐይን ጐላ ጐላ ብሎ እንዲታይና ውበት እንዲ ኖረው የሚያደርግ ጥቍር ዱቄት ነው (2ነገ9፥30፤ ሕዝ23፥40 ይመ):: ***የተወዳጀሻቸው፤*** ለዚህ የገባው አቻ የዕብራይስጥ ቃል ከዚህ የሚገኘው በሕዝ23፥5፡7፡9፡12፡16፡20 ላይ ብቻ ሲሆን፣ የሁለት አመንዝራ እኅትማማቾችን የሰማርያንና የኢየሩሳሌምን (የ2፥20፤ 3፥7 ማብ ይመ) ከባዕድ አገሮችና ከአማልክታቸው ጋር "በዝሙት" መዳራት ለማመልከት ነው:: ***ነፍስሽን ሊያጠፉ ይፈልጋሉ፤*** ሐሳባቸው ሁሉ የተነሣሣው አንቺን ለመግደል ብቻ ነው (ቍ31 ይመ)::

4፥31 ***የጽዮን ሴት ልጅ፤*** ኢየሩሳሌምና ነዋሪዎቿ በሰውኛ ዘይቤ ቀርበዋል (6፥2፡23 ይመ):: ***እጇን ዘርግታ፤*** ርዳታ ለማ ግኘት ስትጸልይ ለማለት ነው (ኢዮ11፥13 ይመ)::

*5፥1-31፤* ኤርምያስ፣ የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን ሕዝብ ክፋት ቁልጭ አድርጎ መግለጹን እንደ ገና በዚህ ክፍል ይጀም ራል::

*5፥1፤* ሶፎ1፥12 ይመ:: እግዚአብሔር፣ በእስራኤል ውስጥ "እስቲ አንድ ጻድቅ ሰው ካገኙሁ ፈልጉ" በማለት እያንዳንዱን ሰው ይጠይቃል፤ ጥያቄውም ከተማዋ በሞላ በምግባረ ብልሹነት የተጥለቀለቀች መሆን ገልጦ ለማሳየት ነው (መዝ14፥1-3፤ ኢሳ 64፥6-7፤ ሆሴ4፥1-2፤ ሚክ7፥2 ይመ):: ***ብታገኙ ... እምራታለሁ፤*** ዘፍ18፥26-32 ይመ::

5፥2 ***ሕያው እግዚአብሔርን፤*** 4፥2 ይመ፤ በተጨማሪም ዘፍ42፥15 እና ማብ ይመ:: ***የሚምሉት በሐሰት ነው፤*** ዘሌ19፥12 ላይ ያለውን በመጣስ (የዘፀ20፥7 ማብ ይመ):: የዕብራይስጡ ሐረ

[3] *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ዐይኖችህ እውነትን
  አይመለከቱምን?
 አንተ መታሃቸው፤ እነርሱ ግን
  አልተሰማቸውም፤
አደቀቅሃቸው፤ እነርሱ ግን አልታረሙም፤
 ፊታቸውን ከድንጋይ ይልቅ አጠነከሩ
 በንስሓ ለመመለስም አልፈለጉም።
[4] እኔም በልቤ እንዲህ አልሁ፤ "እነዚህ
  ድኾች ናቸው፤
 ሞኞች ናቸው፤
*የእግዚአብሔርን* መንገድ፣
 የአምላካቸውን ሕግ አላወቁምና።
[5] ስለዚህ ወደ ታላላቆቹ እሄዳለሁ፤
 ለእነርሱም እናገራለሁ፤
በእርግጥ እነርሱ *የእግዚአብሔርን*
  መንገድ፣
 የአምላካቸውንም ሕግ ያውቃሉና።"
ነገር ግን እነርሱም ቢሆኑ ያው እንደዚያው
  ቀንበሩን ሰብረዋል፤
 እስራቱንም በጥሰዋል።
[6] ስለዚህ አንበሳ ከዱር ወጥቶ
  ይሰባብራቸዋል፣
 የበረሓ ተኵላም ይበጫጭቃቸዋል፤
ብቅ የሚለውን ሰው ሁሉ ለመገንጠል፣
 ነብር በከተሞቻቸው ዙሪያ ያደባል፤
ዐመፃቸው ታላቅ፣
 ክሕደታቸው ብዙ ነውና።
[7] "ታዲያ፣ እንዴት ይቅር ልልሽ እችላለሁ?
 ልጆችሽ ትተውኛል፤
እውነተኛውን አምላክ ትተው አማልክት
  ባልሆኑት ምለዋል፤
 እስኪጠግቡ ድረስ መገብኋቸው፤
እነርሱ ግን አመነዘሩ፤
 ወደ ጋለሞቶችም ቤት ተንጋጉ።
[8] እንደ ተቀለበ ብርቱ ድንጕላ ፈረስ ሆኑ፤
 እያንዳንዱም የሌላውን ሚስት ተከትሎ
  አሽካካ።
[9] ስለ እነዚህ ነገሮች አልቀጣቸውምን?"
  ይላል *እግዚአብሔር*።
 "እኔ ራሴ እንደዚህ ዐይነቱን ሕዝብ፣
  አልበቀልምን?
[10] "ወደ ወይን አትክልቷ ስፍራ ገብታችሁ
  አበላሹት፤
 ነገር ግን ፈጽማችሁ አታጥፉት፤
ቅርንጫፎቿን ገንጥሉ፤
 *የእግዚአብሔር* አይደሉምና፤
[11] የእስራኤል ቤትና የይሁዳ ቤት፣
 ፈጽመው ከድተውኛል፤"
  ይላል *እግዚአብሔር*።
[12] *በእግዚአብሔር* ላይ ሐሰትን ተናገሩ፤
 እንዲህም አሉ፤ "እሱ ምንም
  አያደርግም!
ክፉ ነገር አይደርስብንም፤
 ሰይፍም ራብም አናይም፤
[13] ነቢያቱ ነፋስ እንጂ ሌላ ነገር አይደሉም፤
 ቃሉም በውስጣቸው የለም፤
 ያሉት ሁሉ በእነርሱ ላይ ይመለስ።"
[14] ስለዚህ *የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር* እንዲህ
ይላል፤
"ሕዝቡ ይህን ቃል ስለ ተናገረ፣
 ቃሌን በአፍህ ውስጥ የሚፋጅ እሳት፣
ይህንም ሕዝብ ማገዶ አደርጋለሁ፤
 እሳቱም ይበላቸዋል።
[15] የእስራኤል ቤት ሆይ፣" ይላል
  *እግዚአብሔር*፤
 "ከሩቅ ሕዝብን አመጣባችኋለሁ፤
ጥንታዊና ብርቱ፣
 ቋንቋውን የማታውቁት፣ ንግግሩንም
  የማትረዱት ሕዝብ ነው።

5፥3 ዘሌ26፥23፤ 2ዜና28፥22፤16፥9፤ ኢሳ1፥5፤9፥13፤ኤር7፥26፤19፥15፤ሕዝ2፥4-5፤3፥8-9፤36፥26፤አሞ4፥16፤ዘካ7፥11፡12
5፥4 ቍ21፤ምሳ10፥21፤ኢሳ1፥3፤ኤር4፥22
5፥5 ኤር2፥20፤ ሚክ3፥1፡9፤
5፥6 ዘሌ26፥22፤ መዝ17፥12፤ኤር14፥7፤30፥14፤ሆሴ13፥7
5፥7 ዘኍ25፥1፤ዘዳ32፥21፤ኢሱ23፥7፤ ኤር2፥11፤13፥27፤ 16፥20፤ገላ 4፥8
5፥8 ኤር29፥23፤ ሕዝ22፥11፤33፥26
5፥9 ቍ29፤ኢሳ57፥6፤ ኤር9፥9
5፥10 ኤር 4፥27፤ አሞ 9፥8
5፥11 1ነገ19፥10፤ መዝ73፥27፤ኢሳ24፥16
5፥12 ኢሳ28፥15፤ ኤር14፥13፤23፥17፤ 27፥8
5፥13 2ዜና36፥16፤ ኢዮ6፥26፤ኤር14፥15
5፥14 መዝ39፥3፤ ኢሳ1፥31፤ኤር23፥29፤ሆሴ6፥5
5፥15 ዘዳ11፥7፤ዘዳ28፥49፤2ነገ24፥2፤ ኢሳ28፥11

ግ በ7፥9 ላይም "በሐሰት ትምላላችሁ" ተብሎ ተተርጕሞአል።

5፥3 *አልታረሙም*፤ 2፥30 ይመ። *ፊታቸውን ከድንጋይ ይልቅ አጠነከሩ፤* ስሜትን በሚነካ ሁኔታ ዐመፅን ለመግለጽ የገባ አባባል ነው (ሕዝ3፥7-9 ይመ)።

5፥4 *ድኾች*፤ ሐሳባቸው ያረፈው በመሠረታዊውና ሥጋዊ በሆነው ጕዳይ ላይ በመሆኑ (ከ39፥10፤ 40፥7 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ስለ እግዚአብሔር ቃልና ስለ መንገዱም አላወቁም፤ አልተነገራቸውም። *ሞኞች*፤ 4፥22 ይመ፤ በተጨማሪም ዘኍ12፥11 ይመ፤ የዕብራይስጡ ቃል፣ "ሞኞች" ለሚለው "ግብረ ገብነት የጐደላቸው" የሚል ትርጕም ያዘለ ነው። *የአምላካቸውን ሕግ አላወቁምና*፤ ከሰማይ ወፎች እንኳ ያነሰ ዕውቀት ያላቸው ናቸው (8፥7ይመ)።

5፥5 *ታላላቆቹ፤* ቃል በቃል፣ "ትልልቆቹ" ተብሎ ሊተረጐም ይችላል። ሁሉንም ነገር የማድረግና የማግኘት ዕድል ያላቸው ሰዎች ቢሆኑም እንኳ፣ በሕዝቡ መካከል ከሚገኙት ከመጨረሻዎቹ ድኾች የተሻለ የጽድቅ ሕይወት አልነበራቸውም። *ቀንበሩን ... እስራቱንም*፤ የ2፥20 ማብ ይመ።

5፥6 *አንበሳ ... ተኵላም ... ነብር*፤ ዘሌ26፥22፤ ሕዝ14፥15 ይመ፤ ከ2ነገ 17፥25-26 ጋር ያነጻጽሩ። *ያደባል*፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በ1፥12 ላይ "እተጋለሁ" ተብሎ ተተርጕሞአል። *ክሕደታቸው*፤ 2፥19፤ 3፥22፤ 14፥7 ይመ፤ ቃሉ ተደጋጋሚ ከሓዲነትን ያመለክታል።

5፥7 *እንዴት ይቅር ልልሽ እችላለሁ?* ቍ1 ይመ። *እውነተኛውን አምላክ ትተው አማልክት*፤ በጣዖታት ማለት ነው (2፥11 ይመ)። *መገብኋቸው፤ እነርሱ ግን፤* ዘዳ32፥15-16፤ ሆሴ2፥8 ይመ። *አመነዘሩ፤* የ2፥20 ማብ ይመ።

*5፥8፤* የአምልኮት ምንዝርና (ቍ7፤ አሞ2፥7 ይመ) ወደ ተለመደው የማመንዘር ተግባር ይመራል፤ ይህም የእግዚአብሔርን ትእዛዝ መጣስ ነው (ዘፀ20፥14፡17 ይመ)። *እንደ ተቀለበ ... ድንጕላ ፈረስ*፤ 13፥27፤ 50፥11፤ ሕዝ23፥20 ይመ።

5፥10 *ገብታችሁ*፤ የተነገረው ለእስራኤል ጠላቶች ነው (ቍ15 ይመ)። *የወይን አትክልቷ ስፍራ፤* የወይን ተክልና የወይን ተክል ቦታ ብዙውን ጊዜ እስራኤልን የሚያመለክቱ ናቸው (የ2፥21፤ የኢሳ5፥1 ማብ ይመ)። *ፈጽማችሁ አታጥፉት*፤ ቍ18 ይመ፤ በተጨማሪ የ4፥27 ማብ ይመ። *ቅርንጫፎቿን ገንጥሉ*፤ ኢሳ18፥5፤ ዮሐ15፥2፡6 ይመ። *የእግዚአብሔር አይደሉምና*፤ ሆሴ 1፥9 ይመ።

*5፥11፤* የ3፥7 ማብ ይመ።

5፥12 *ምንም አያደርግም*፤ ክፉም ሆነ በጎ ነገርለማለት ነው (ሶፎ1፥12 ይመ)። *ሰይፍም ራብም*፤ ኤርምያስ በአንድነት ከሚጠቅሳቸው ሦስት ነገሮች "ሰይፍ፣ ራብና መቅሠፍት" (የ14፥13 ማብ ይመ) ውስጥ፣ ሁለቱን እዚህ ላይ አበክሮ ያሰተዋውቃል።

5፥13 *ነቢያቱ ነፋስ እንጂ ሌላ ነገር አይደሉም*፤ እንደ ጣዖታቱ ምስል ማለት ነው (ኢሳ41፥29 ይመ)። *ያሉት ሁሉ በእነርሱ ላይ ይመለስ*፤ የ4፥29 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም መዝ 7፥16፤ 54፥5 ይመ።

5፥14 *ቃሌን በአፍህ ውስጥ የሚፋጅ እሳት*፤ በሐሰተኛ ነቢያት አፍ አንጻሩ የእግዚአብሔር ቃል ካለመኖሩ ጋር የሚነጻጸር ነው (ቍ13)። *ማገዶ፤* የኢሳ1፥31 ማብ ይመ።

5፥15 *ከሩቅ ሕዝብን*፤ የ4፥16 ማብ ይመ። *ጥንታዊና ብርቱ ... ሕዝብ፤* ሁለት ሺህ ዓመታትና ከዚያም በላይ ታሪክ ያላትን ባቢሎንን ለማለት ነው። *ቋንቋውን የማታውቁት፤* ዘዳ 28፥49 እና ማብ ይመ።

[16]የፍላጻቸው ሰገባ እንደ ተከፈተ
መቃብር ነው፤
ሁሉም ብርቱ ተዋጊዎች ናቸው።
[17]ሰብልህንና ምግብህን ጠራርገው
ይበሉብሃል፤
ወንዶችና ሴቶች ልጆችህን ይውጣሉ፤
በጎችህንና ከብቶችህን ይፈጃሉ፤
የወይን ተክሎችህንና የበለስ ዛፎችህን
ያወድማሉ፤
የታመንህባቸውንም የተመሸጉ ከተሞች፣
በሰይፍ ያጠፉአቸዋል።

[18]"ይሁን እንጂ፣ በዚያን ዘመን እንኳ" ይላል እግዚአብሔር፤ "ፈጽሜ አላጠፋችሁም። [19]ሕዝቡ፣ 'እግዚአብሔር አምላካችን ይህን ሁሉ ነገር ለምን አደረገብን?' ብለው ቢጠይቁ 'እኔን፣ እንደ ተዋችሁኝና በራሳችሁ ምድር ባዕዳን አማልክትን እንዳገለገላችሁ፣ እንደዚሁ የእናንተ ባልሆነ ምድር ባዕዳንን ታገለግላላችሁ' ትላቸዋለህ።

[20]"በያዕቆብ ቤት ይህን አስሙ፣
በይሁዳም እንዲህ ብላችሁ ዐውጁ፤
[21]እናንት ዐይን እያላችሁ የማታዩ፣
ጆሮ እያላችሁ የማትሰሙ፣
ሞኞችና የማታስተውሉ ሰዎች
ይህን ስሙ፤
[22]ልትፈሩኝ አይገባችሁምን?" ይላል
እግዚአብሔር፤
"በእኔ ፊት ልትንቀጠቀጡስ አይገባምን?
ለዘላለም ዐልፎት መሄድ እንዳይችል፣
አሸዋን ለባሕር ድንበር አደረግሁ፤
ማዕበሉ እየጋለበ ቢመጣ ከዚያ አያልፍም፤
ሞገዱ ቢጮኽም ሊያቋርጠው
አይችልም።
[23]ይህ ሕዝብ ግን የሸፈተና እልከኛ
ልብ አለው፤
መንገድ ለቆ ሄዶአል፤
[24]በልባቸውም፣
'የፊተኛውንና የኋለኛውን ዝናብ
በጊዜው የሚያዘንበውን፣
መከርን በወቅቱ የሚያመጣልንን፣
አምላካችንን እግዚአብሔርን እንፍራ'
አላሉም።
[25]በደላችሁ እነዚህን አስቀርቶባችኋል።
ኀጢአታችሁ መልካሙን ነገር
ከልክሎአችኋል።

[26]"በሕዝቤ መካከል ክፉ ሰዎች አሉና፤
ወፍ እንደሚያጠምዱ ሰዎች፣
ወጥመድ ዘርግተው ሰው እንደሚይዙ
ሰዎችም ያደባሉ።
[27]ወፎች እንደሞሉት ጐጆ፣
ቤታቸው በማጭበርበር የተሞላ ነው፤
ባለጠጎችና ኀያላን ሆነዋል፤
[28]ወፍረዋል፤ ሰብተዋልም።
ክፋታቸው ገደብ የለውም፤
ወላጅ የሌላቸው ፍትሕ እንዲያገኙ
አልቆሙላቸውም፤
ለድኾችም መብት አልተከራከሩም።
[29]ስለ እነዚህ ነገሮች ልቀጣቸው
አይገባኝምን?"
ይላል እግዚአብሔር።
እንዲህ ዐይነቶቹን ሕዝብ፣
እኔ ራሴ ልበቀላቸው አይገባኝምን?

[30]"የሚያስፈራና የሚያስደነግጥ ነገር፣
በምድሪቱ ላይ ሆኖአል፤
[31]ነቢያት በሐሰት ትንቢት ይናገራሉ፤
ካህናት በነቢያቱ ምክር ያስተዳድራሉ፤
ሕዝቤም እንዲህ ያለውን ይወዳሉ፤
ፍጻሜው ሲደርስ ግን ምን ታደርጉ
ይሆን?

## የኢየሩሳሌም መከበብ

6 "እናንት የብንያም ልጆች፤ ክፉ ነገር፣ ታላቅም ጥፋት ከሰሜን ድንገት

5፥16 ኢዮ 39፥23
5፥17 ዘሌ26፥16፡25፤ዘኍ16፥14፤ዘዳ28፥31፡32፡33፤ኢሱ10፥20፤ኢሳ1፥7፤ኤር8፥13፡16፤30፥16፤50፥7፡17፤ሆሴ2፥12
5፥18 ኤር 4፥27
5፥19 ዘዳ 4፥28፤28፥48፤1ነገ9፥9፤ኤር2፥8፤15፥14፤16፥13፤17፥4
5፥20 ኤር 4፥5
5፥21 ቍ4፤ዘዳ29፥4፤32፥6፤ኢሳ6፥10፤42፥20፤ኤር4፥22፤ሕዝ12፥2፤ዕን2፥18፤ማቴ13፥15፤ማር8፥18
5፥22 ዘፍ1፥9፤ ዘዳ28፥58፤ኢዮ4፥14፤መዝ46፥3፤ኢሳ64፥2
5፥23 ዘዳ 21፥18፤መዝ14፥3
5፥24 ዘፍ8፥22፤ዘሌ26፥4፤ዘዳ 6፥24፤2ሳሙ1፥21፤ሐሥ14፥17፤ያዕ5፥7
5፥25 መዝ 84፥11
5፥26 መዝ 10፥8፤መክ9፥12፤ኤር9፥8፤ሆሴ5፥1፤ሚክ7፥2፤ማቴ7፥15
5፥27 ኤር 8፥5፤9፥6፤12፥1
5፥28 ዘፀ22፥21-24፤ዘዳ32፥15፤መዝ82፥3፤ኢሳ1፥23፤ኤር7፥6፤ሕዝ16፥49፤አሞ5፥12፤ዘካ 7፥10፤
5፥29 ኢሳ57፥6
5፥30 ቍ30-31፤ኤር18፥13፤23፥14፤ሆሴ6፥10
5፥31 ቍ1፤ሰቆ4፥13፤ሆሴ9፥5፤ሚክ2፥11
6፥1 ዘኍ10፥7፤2ዜና11፥6፤ነህ3፥14፤ኤር4፥6፡21፤አሞ1፥1

5፥16 *እንደ ተከፈተ መቃብር፤* አለመርካትን፣ ጥፋትንና ሞትን የሚያመለክት አባባል ነው (መዝ5፥9፤ ምሳ30፥15-16 ይመ)።

5፥17 *ወንዶችና ሴቶች ልጆችህን ይውጣሉ፤* ለባሪያነት መውሰዳቸውን ወይም በጦርነት ማለቃቸውን (10፥25 ይመ) ለመግለጽ ነው። *የታመንህባቸውንም የተመሸጉ ከተሞች፤* የ4፥5 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዘዳ28፥52 ይመ።

*5፥18፤* ቍ10 ይመ፤ እንዲሁም የ4፥27 ማብ ይመ።

5፥21 *ይህን ስሙ፤* የ2፥4 ማብ ይመ። *ሞኞችና የማታስተውሉ፤* 4፥22 ይመ፤ የዕብራይስጡ ቃል "ሞኞች" ለሚለው፣ "ግብረ ገብነት የጐደለው" የሚል ትርጕም አዝሎአል። *ዐይን እያላችሁ ... የማትሰሙ፤* የኢሳ6፥10 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዘዳ29፥4፤ መዝ115፥4-8፤ 135፥15-18 ይመ።

5፥22 *ልትፈሩኝ፤* የዘፍ20፥11 ማብ ይመ። *ለባሕር ድንበር፤* ኢዮ38፥8-11፤ መዝ104፥6-9 ይመ።

*5፥23፤* ባሕር እንኳ እግዚአብሔር የወሰነለትን ድንበር ጥሶ አያልፍም፤ የእግዚአብሔር ሕዝብ ግን ከተፈቀደላቸው ገደብ በላይ ሄደዋል።

5፥24 *የሚያዘንበውን ... እግዚአብሔርን፤* ቍ7 እና ማብ ይመ፤ *የፊተኛውንና የኋለኛውን ዝናብ፤* 3፥3 ይመ፤ በተጨማሪም የዘዳ11፥14 ማብ ይመ። *መከርን በወቅቱ፤* ምናልባት በፋሲካ በዓልና በበዓለ ኀምሳ መካከል ያሉት ሰባት ሳምንታት ሊሆኑ ይችላሉ (ዘሌ23፥15-16 ይመ)።

5፥26 *ወጥመድ፤* የዕብራይስጡ ቃል በቀሙ ሲተረጐም፣ "አጥፊ" (ለምሳሌ:- ዘፀ12፥23 ይመ) ወይም "ጥፋት" (ለምሳሌ:- ሕዝ21፥31 ይመ) ማለት ነው። *ሰው፤* ንጹሑን ሰው (ኢሳ29፥21 ይመ)፣ ቅዱሳንንና ቅን ሰዎችን ማለት ነው (ሚክ7፥21 ይመ)።

5፥27 *ጐጆ፤* ከሸምበቆ እንጨት የተሠራ ማጥመጃ ማለት ነው፤ ይህ የዕብራይስጥ ቃል በአሞ8፥1-2 ላይ "ዕንቅብ" ተብሎ ተተርጕሞአል። *በማጭበርበር፤* በማወናበድና በማታለል የተገኘ ሀብት ማለት ነው (ዕን2፥6 ይመ)።

5፥28 *ወፍረዋል፤ ሰብተዋልም፤* በሀብት መደራጀትን ለማመልከት የገባ አባባል ነው (ዘዳ32፥15 ይመ)። *ክፋታቸው ገደብ የለውም፤* መዝ73፥7 ይመ። *ፍትሕ እንዲያገኙ አልቆሙላቸውም፤* ክፉ ሰዎች ለማድረግ ያልፈለጉትን፣ እግዚአብሔር ያደርጋል (ዘዳ10፥18 ይመ)፤ ክፉዎች የተዉትን በጎ ነገርም፣ እግዚአብሔርን በእውነት የሚያውቁትና የሚያገለግሉት ያደርጋሉ (22፥16፤ ያዕ1፥27 ይመ)።

*5፥29፤* የቍ9 ሐሳብ እዚህ ላይ ተደግሞአል።

*5፥31፤* 1፥18 እና ማብ ይመ። *በሐሰት ትንቢት ይናገራሉ፤* 20፥6 ይመ (ብዙውን ጊዜ በድፍረት በእግዚአብሔር ስም ይናገራሉ፤ 23፥25፤ 27፥15፤ 29፥9 ይመ)። *ሕዝቤም እንዲህ ያለውን ይወዳሉ፤* የአሞ4፥5 ማብ ይመ።

*6፥1-30፤* ባቢሎን በኢየሩሳሌም ላይ የምታደርሰው ጥቃት ለነቢዩ ከወዲሁ ይታየዋል።

*6፥1፤* በቍ1-3 ላይ የሚናገረው ጌታ ነው። ቍ1 ላይ የተነገረው ሐሳብ 4፥6ን ያስታውሰናል (የ4፥6 ማብ ይመ)። በ4፥6

ይመጣልና፣
ከኢየሩሳሌም ሸሽታችሁ አምልጡ፤
በቴቁሔ መለከትን ንፉ፤
በቤትሐካሪም ላይ ምልክት ከፍ
አድርጋችሁ አሳዩ።
2ውብና ሽሙንሙን የሆነችዋን፣
የጽዮንን ሴት ልጅ አጠፋታለሁ።
3እረኞች መንጎቻቸውን ይዘው
ይመጡባታል፤
ድንኳናቸውን በዙሪያዋ ይተክላሉ፤
እያንዳንዳቸውም በየአቅጣጫቸው
መንጋቸውን ያሰማራሉ።"
4"በእርሷ ላይ ጦርነት ዐውጁ፤
ተነሡ! በቀትር አደጋ እንጣልባት፤
ወይ ጉድ! ቀኑ እኮ መሸብን!
ጥላው ረዘመ።
5እንግዲህ ተነሡ በሌሊት እናጥቃት፤
ምሽጎቿንም እንደምስስ!"

6የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ
ይላል፤

"ዛፎቹን ቍረጡ፤
በኢየሩሳሌም ዙሪያ የዐፈር ድልድል
ሥሩ።
ይህቺ ከተማ ቅጣት ይገባታል፤
ግፍን ተሞልታለችና።
7የውሃ ጕድጓድ ውሃ እንደሚያመነጭ፣
እርሷም እንዲሁ ክፋቷን ታፈልቃለች።
ዐመፅና ጥፋት በውስጧ ይስተጋባል፤
ሕመሟና ቍስሏ ዘወትር ይታየኛል።
8ኢየሩሳሌም ሆይ፤ ተጠንቀቂ፤
አለበለዚያ ከአንቺ ዘወር እላለሁ፤
ማንም ሊኖርባት እስከማይችል ድረስ፣
ምድርሽን ባዶ አደርጋለሁ።"

9የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ
ይላል፤

"የወይን ፍሬ ተሟጦ እንደሚቃረም፣
ከእስራኤል የተረፉትን እንዲሁ
ይቃርሟቸው።
ወይን ለቃሚ እንደሚለቅም፣
እጅህን ወደ ቅርንጫፎቹ ደጋግመህ
ዘርጋ።"

10ለማን ልናገር? ማንን ላስጠንቅቅ?
ማንስ ይሰማኛል?
እነሆ፣ ጆሮዎቻቸው አልተገረዙምና፣[ሀ]
መስማት አይችሉም።
*በእግዚአብሔር* ቃል ይሣለቃሉ፤
ደስም አይሰኙበትም።
11በእነርሱ ላይ *በእግዚአብሔር* ቍጣ
ተሞልቻለሁ፤
በውስጤም ልይዘው አልቻልሁም።
"መንገድ ላይ በሚገኙ ሕፃናት፣
በተሰበሰቡ ወጣቶችም ላይ አፍስሰው፤
ባልም ሚስትም፣

[ሀ]10 ወይም *ጆሮዎቻቸው ተደፍነዋል*

6፥2 መዝ9፥14፤ ሰቆ4፥5
6፥3 2ነገ25፥4፤ኤር 12፥10፤ሉቃ19፥43
6፥4 ኤር15፥8፤ 22፥7
6፥6 ዘዳ20፥19-20፤ 28፥33፤2ሳሙ20፥15፤ ኤር25፥38፤32፥24፤ 52፥4፤ሕዝ26፥8፤ሶፎ 3፥1
6፥7 መዝ55፥9፤ኢሳ 58፥4፤ኤር20፥8
6፥8 ሕዝ23፥18
6፥9 ዘፍ45፥7
6፥10 ኢሳ 42፥20፤ ኤር4፥4፤7፥13:24፤ 15፥10:15፤20፥8፤ 35፥15፤ሐሥ7፥51
6፥11 2ዜና36፥17፤ ኢዮ32፥20፤ኢሳ40፥ 30፤ኤር7፥20፤15፥17 ፤20፥9፤ ሰቆ2፥21

ላይ የተሰጠው ትእዛዝ ወደ ኢየሩሳሌም ገብተው እንዲጠለሉ ሲሆን፣ እዚህ ላይ ግን ሕዝቡ ከኢየሩሳሌም ሸሽተው እንዲወጡ ነው፤ ይኸውም የተቀደሰችው ከተማም ሆነች ሌላ ማንኛውም ስፍራ ከወራሪዎቹ ሊያመልጥ ወይም ሊሰወር ስለማይችል ነው። *የብንያም፣* ከኢየሩሳሌም በስተ ሰሜን ለዚሁ ነገድ የተከለለ የይሁዳ አዋሳኝ ስፍራ ነበር። ኤርምያስ ራሱ ከዚሁ ከብንያም ክልል የመጣ ነበር (1፥1 ይመ)። *በቴቁሔ ... ንፉ፤* በዕብራይስጡ "ንፉ" ለሚለው የገባው ቃል "ቲቁህ" ስለ ሆነ፣ በከተማይቱ ስምና መለከት በመንፋት መካከል የቃላት ጨዋታ እንዳለ ያሳያል። ቴቁሔ የነቢዩ የአሞጽ ትውልድ ስፍራ ነበረች፤ የምትገኘውም ከኢየሩሳሌም በስተ ደቡብ ሃያ ኪሎ ሜትር ላይ ነበር። *ምልክት ከፍ አድርጋችሁ አሳዩ፤* በዚህ ሐረግ ውስጥ፣ በዕብራይስጡ አገባብ፣ በከተማይቱ ስምና "ምልክት በማንሣት" መካከል የቃላት ጨዋታ አለ። ("ምልክት ማንሣት" ማለት እሳት አንድዶ ጢስ ማሳየት ነበር፤ መሳ20፥38:40 ይመ)፤ በ4፥6 ላይ ጥቅም ላይ የዋለው ቃል ግን በዕብራይስጡ ከዚህ የተለየ ነው። *በቤትሐካሪም፤* ይህች ከተማ ከዚህ ሌላ ተጠቅሳ የምትገኘው በነህ3፥14 ላይ ብቻ ነው (የዚያን ማብ ይመ)። *ጥፋት ከሰሜን፤* 1፥14 እና ማብ ይመ።

6፥2 *አጠፋታለሁ፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ ተመሳሳይ ትርጕም በመያዝ በሆሴ4፥5 ላይም ገብቶ ይገኛል። *የጽዮንን ሴት ልጅ፤* ቍ23 ይመ፤ በተጨማሪም የ4፥31 ማብ ይመ። *ሽሙንሙን፤* በኢሳ47፥1 ላይ የባቢሎን ከተማ ለመግለጽ ገብቶ አል።

*6፥3፤* 1፥15 ይመ። *እረኞች መንጎቻቸውን ይዘው፤* ነገሥታት (የ2፥8 ማብ ይመ) ከሰራዊቶቻቸው ጋር ማለት ነው። *እያንዳን ዳቸውም በየአቅጣጫቸው፤* ይህ ሐረግ በተመሳሳይ አገባብ በዘኍ2፥17 ላይ ይገኛል። ያሰማራሉ፣ ሣር ያስግጣሉ፤ ወይም መሬቱን ግጥጥ ብሎ እስኪታይ ድረስ አስበልተው ያበላሹታል።

*6፥4፤* በቍ4-5 የሚነጋገሩት ወራሪዎቹ ናቸው። *ዐውጁ፤* ቃል በቃል ሲታይ፣ "ተለዩ"፣ "ተቀደሱ" የሚል ትርጕም አለው (በኢል3፥9፤ በሚክ3፥5 ላይም እንደዚሁ)። የጥንት ጦርነቶች ሃይማኖታዊ አንድምታ ስለ ነበራቸው ወታደሮች በመንፈስና በወታደራዊ ብቃት ራሳቸውን ማስታጠቅ ነበረባቸው (ዘዳ20፥2-4፤ 1ሳሙ25፥28 ይመ)። *በቀትር፤* በዚያን ጊዜ የተለመደው ጠላትን የማጥቂያ ጊዜ ማለዳ ላይ ነበር፤ እዚህ ላይ ቀትር የተመረጠበት ምክንያት፣ ሳይታሰብ ደርሶ አደጋ ለመጣል ነው።

6፥5 *በሌሊት፤* ሲያጠቁ የዋሉት ወታደሮች ሌሊት ተኝተው ዐድረው በማግስቱ በጠላት ከተማዋን መክበብ ነበረባቸው፤ ሌሊትም ጭምር ለማጥቃት መፈለጋቸው፣ ወኔ እንዳላቸው ያሳያል።

*6፥6፤* እግዚአብሔር ስለ ባቢሎናውያን ሰራዊት መምጣት ይናገራል። *የዐፈር ድልድል ሥሩ፤* የኢየሩሳሌምን ቅጥር ለማፈራረስ እንዲረዳቸውና መወጣጫ መሰላል ዘርግተው ወደ ከተማዋ መግባት እንዲችሉ ነው (33፥4 ይመ)። *ግፍን፤* በራሷ ሕዝብ ላይ የሚፈጸም ነው (የኢሳ30፥12 ማብ ይመ)።

6፥7 *ሕመሟና ቍስሏ፤* ኢየሩሳሌም መንፈሳዊ መላሸቅና የጤና መታወክ ይደርስባታል (ቍ14 ይመ)፤ ይሁን እንጂ አታውቀውም።

6፥8 *ተጠንቀቂ፤* ላቅ ያለውን የጥበብ ክፍል ያሳያል (ቍ10፤መዝ2፥10 ይመ)። *ዘወር እላለሁ፤* በኢየሩሳሌም በማዘንና ተስፋ በመቍረጥ። *ማንም ሊኖርባት እስከማይችል ድረስ ... ባዶ፤* 22፥6 ይመ።

6፥9 *ይቃርሟቸው፤* የሩት 2፥2፤ የኢሳ17፥5 ማብ ይመ። *የተረፉትን፤* 11፥23፤ 23፥3፤ 31፥7፤ 40፥11:15፤ 42፥2:15:19፤ 43፥5፤ 44፥7:12:14:28፤ 50፥20 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ 10፥20-22 ማብ ይመ። *ተሟጦ፤* ጨርሶ ከማጥፋት መለስ ያለ ርምጃ ነው (4፥27፤ 5፥10:18፤ 30፥11፤ 46፥28 ይመ)። *ወይን* እስራኤልን ያመለክታል (2፥21 እና ማብ፤ 5፥10 ይመ)።

*6፥10፤* እዚህ ላይ የሚናገረው ኤርምያስ ራሱ ነው። *ላስጠንቅቅ፤* የቍ8 ማብ ይመ። *ጆሮዎቻቸው አልተገረዙምና፤* ጆሮአቸው ተደፍኖአል ማለት ነው፤ 4፥4 እና ማብ ይመ። "የጆሮ መገረዝ" የሚለው ዘይቤ ከዚህ ሌላ የሚገኘው፣ በሐሥ 7፥51 ላይ ብቻ ነው።

*6፥11፤* እዚህ ላይ ነቢዩ ከተናገረ በኋላ፣ እግዚአብሔር ቀደም ሲል የጀመረውን ቃል መስማቱን ይቀጥላል (እስከ ቍ 23)። *በ... ቍጣ ተሞልቻለሁ፤* 25፥15 ይመ። *ሕፃናት ... ወጣቶችም ... ባልም፣ ሚስትም... ያረጁና፤* ከትንሽ እስከ ትልቅ ከፍርድ አያመልጡም (ቍ13 ይመ)። *መንገድ ላይ፤* የልጆች መጫወቻ ስፍራ ማለት ነው (9፥21፤ ዘካ8፥5 ይመ)።

*6፥12-15፤* በ8፥10-12 ላይ ያለው ሐሳብ ከሞላ ጎደል ቃል በቃል ተደግሞአል።

ያረጁና የጃጁም አያመልጡም።
[12]በምድሪቱ በሚኖሩት ላይ፣
እጄን በምዘረጋበት ጊዜ፣
ዕርሻቸውና ሚስቶቻቸው ሳይቀሩ፣
ቤቶቻቸው ለሌሎች ይሆናሉ፤"
ይላል እግዚአብሔር።
[13]"ከትንሹ እስከ ትልቁ ሰው፣
ሁሉም ለጥቅም የሚስገበገቡ ናቸው፤
ነቢያቱም ካህናቱም ሳይቀሩ፣
ሁሉም ያጭበረብራሉ።
[14]የሕዝቤን ቍስል እንደ ቀላል ቈጠሩ፣
እንዲፈወስም ተገቢውን እንክብካቤ
አላደረጉለትም፤
ሰላምም ሳይኖር፣
'ሰላም፣ ሰላም' ይላሉ።
[15]ስለ ጸያፉ ተግባራቸው ዐፍረዋል እንዴ?
ኧረ ጨርሶ ዕፍረት የላቸውም!
ዕፍረት ምን እንደ ሆነ እንኳ አያውቁም፤
ስለዚህ ከሚወድቁት ጋር ይወድቃሉ፤
በምቀጣቸውም ጊዜ ይዋረዳሉ፤"
ይላል እግዚአብሔር።

[16]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"መንታ መንገድ ላይ ቁሙ፣ ተመልከቱም፤
መልካሚቱ፣ የጥንቷን መንገድ ጠይቁ፤
በእርሷም ላይ ሂዱ።
ለነፍሳችሁ ዕረፍት ታገኛላችሁ፤
እናንተ ግን፣ 'በእርሷ አንሄድም'
አላችሁ።
[17]ጠባቂዎችን አቆምሁላችሁ፤
'የመለከትንም ድምፅ ስሙ' አልኋችሁ፤
እናንተ ግን፣ 'አንሰማም' አላችሁ።
[18]እንግዲህ ሕዝቦች ሆይ ስሙ፤
እናንተም ምስክሮች ምን
እንደሚገጥማቸው እስተውሉ።
[19]ምድር ሆይ፤ ስሚ፤

6፥12 ዘዳ28፥30፤ 1ነገ11፥4፤ ኢሳ5፥25፤ ኤር8፥10፤21፥5፤ 29፥23፤32፥21፤38፤ 22፤43፥6፤44፥9፤15፤ ሕዝ6፥14፤35፥3፤ሚክ 2፥4፤ሶፎ1፥4
6፥13 ኢሳ56፥11፤ ኤር2፥29፤ሰቆ4፥13
6፥14 ኢሳ30፥10፤ ኤር4፥10
6፥15 2ዜና25፥16፤ ኤር3፥3፤8፥10-12፤ 27፥15፤ሚክ3፥7፤ዘካ 13፥4
6፥16 ኢሱ1፥13፤ 1ነገ8፥36፤መዝ119፥ 3፤ኢሳ11፥10፤ኤር 18፥15፤ማቴ11፥29
6፥17 ዘፀ20፥18፤ ኢሳ52፥8፤ኤር11፥7-8 ፤ሕዝ33፥4፤ዘካ1፥4
6፥19 ዘዳ4፥26፤ኢሱ 23፥15፤ምሳ1፥31፤ ኤር8፥9፤11፥11፤19፥ 3፤22፥29፤29፥19፤ ሕዝ20፥13፤አሞ 2፥4፤ሚክ1፥2
6፥20 ዘፍ10፥7፤ ዘፀ 30፥23፤መዝ50፥8-10 ፤ኢሳ1፥11፤ኤር7፥21፤ 14፥12፤ሆሴ8፥13፤ 9፥4፤አሞ5፥22፤ሚክ 6፥7-8፤ሚል1፥9
6፥21 ዘሌ 26፥37፤ ኢሳ8፥14
6፥22 ዘዳ 28፥49፤ ኤር 4፥6
6፥23 መዝ 18፥41፤ 93፥3፤ኢሳ10፥32፤ 13፥18፤ኤር4፥29
6፥24 ኢሳ13፥7፤ ኤር4፥19፤31፥50፥ 41-43
6፥25 ኢዮ15፥21፤ መዝ31፥13፤ኤር49፥ 29

ቃሌን ስላላደመጡ፣
ሕጌንም ስለናቁ፣
በዚህ ሕዝብ ላይ የሐሳባቸውን ውጤት፣
ጥፋትን አመጣባቸዋለሁ።
[20]ዕጣን ከሳባ ምድር፣
ጣፋጩ ቅመም ከሩቅ አገር ቢመጣ ምን
ይጠቅመኛል?
የሚቃጠል መሥዋዕታችሁን አልቀበልም፤
ሌላውም መሥዋዕታችሁ ደስ
አያሰኘኝም፤
[21]ስለዚህ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
በዚህ ሕዝብ ፊት መሰናክልን አስቀምጣለሁ፤
አባቶችና ወንዶች ልጆች በአንድነት
ይደናቀፉበታል፤
ጎረቤቶችና ባልንጀሮችም ይጠፋሉ።"
[22]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፤ ሰራዊት፣
ከሰሜን ምድር እየመጣ ነው፤
ከምድር ዳርቻም፣
ታላቅ ሕዝብ እየተነሣሣ ነው።
[23]ቀስትና ጦር ይዘዋል፤
ጨካኞችና ምሕረት የለሽ ናቸው፤
ፈረሶቻቸውን ሲጋልቡ፤
ድምፃቸው እንደተናወጠ ባሕር ነው፤
የጽዮን ልጅ ሆይ፤ ለሰልፍ የታጠቁ
ሆነው፣
ሊወጉሽ ይመጣሉ።"
[24]ስለ እነርሱ ወሬ ደርሶናል፤
ክንዶቻችንም ዝለዋል፤
ጭንቀት ይዞናል፤ እንደምታምጥም
ሴት ሆነናል።
[25]ጠላት ሰይፍ ታጥቆአል፤
በየቦታውም ሽብር ሞልቶአል፤
ስለዚህ ወደ ውጭ አትውጡ፤
በየመንገዱ አትዘዋወሩ።

6፥12 *ዕርሻቸውና ሚስቶቻቸው ... ቤቶቻቸው፤* ዘፀ 20፥17፤ ዘዳ5፥21 ይመ። *ለሌሎች ይሆናሉ፤* በዘዳ28፥30 ላይ እንደተሰጠው ማስጠንቀቂያ፣ ከኪዳን እርግማኖች አንዱ ነው። *በ ... ላይ እጄን በምዘረጋበት ጊዜ፤* ለማጥፋት ነው (15፥6 ይመ)።

*6፥13፤* 1፥18 እና ማብ ይመ።

6፥14 *ቍስል፤* የቍ7 ማብ ይመ። *ሰላምም ሳይኖር፣ 'ሰላም ... '፤* የሐሰተኛና የስግብግብ ነቢያት የተለመደ መልእክት ነው (ሕዝ13፥10፤ ሚክ3፥5 ይመ)። ያም ሆነ ይህ ክፉዎች በሰላም መኖር አይችሉም (ኢሳ48፥22፤ 57፥21)።

6፥16 *የጥንቷን መንገድ፤* የይሁዳ ቀደምት አባቶች የተመላለሱበት እውነተኛው መንገድ ማለት ነው(18፥15፤ ዘዳ32፥7 ይመ)። *በእርሷም ላይ ሂዱ፤* ኢሳ30፥21 ይመ። *ለነፍሳችሁ ዕረፍት ታገኛላችሁ፤* ጌታ ኢየሱስም በማቴ11፥29 ይህን ጠቅሶታል (ኢሳ28፥12 ይመ፤ ከመዝ119፥165 ጋር ያነጻጽሩ)።

6፥17 *ጠባቂዎችን፤* እውነተኞቹን ነቢያት የሚያመለክት ነው (ሕዝ3፥17፤ 33፥7፤ ዕንባ2፥1 ይመ)። *የመለከትን ድምፅ፤* ከተቃረበ አደጋ ለማስጠንቀቅ የሚነፋ ነው (ቍ1 ይመ፤ በተጨማሪም የኢል2፥1 ማብ ይመ)።

6፥18 *ሕዝቦች ሆይ፤ ስሙ፤* ሚክ1፥2 ይመ።

6፥19 *ሕጌንም ስለ ናቁ፤* የሙሴን ሕግ (የኦሪትን ሕግ) አልጠበቁም ማለት ነው (8፥8-9 ይመ)።

6፥20 *ከሳባ፤* ከዐረቢያ አገር በስተ ደቡብ ምዕራብ የሚገኝ ሲሆን፣ የቅመማ ቅመም ንግድ መናኸሪያ ምድር ነበር (ኢሳ60፥6 እና ማብ ይመ። የዕብራይስጡ ቃል በዘፀ30፥23 ላይ "ጣፋጭ ቀረፋ" ተብሎ ተተርጕሞአል። *የሚቃጠል መሥዋዕታችሁን አልቀበልም፤* በአምልኮ ሥርዐት ከሚቀርብ መሥዋዕት ይልቅ የሰው የልብ ዝንባሌና የሕይወት አካሄድ ትልቅ ስፍራ ይሰጠዋል (የኢሳ1፥11-15 ማብ ይመ)።

6፥21 *መሰናክልን፤* ወራሪውን የባቢሎን ሰራዊት ለማለት ነው (ቍ22 ይመ)።

6፥22 *ከሰሜን ምድር፤* የባቢሎንን ምድር ነው (4፥6፤ኢሳ 41፥25እና ማብ ይመ)። *ከምድር ዳርቻም፤* 25፥32፤31፥8 ይመ።

*6፥22-24፤* በ50፥41-43 ላይ ከሞላ ጐደል እንዳለ ቃል በቃል ተደግሞ ይገኛል።

6፥23 *ጦር፤* የዕብራይስጡ ቃል በ1ሳሙ17፥6 ላይ ጭሬ ተብሎ ተተርጕሞአል፤ ዐልፎ ዐልፎም "ጐራዴ" ተብሎ ሊተረጐም እንደሚችል ከሙት ባሕር አካባቢ የተገኘው የታሪክ ማስረጃ ያሳያል። *እንደ ተናወጠ ባሕር፤* ኢሳ5፥30 ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ17፥12 እና ማብ ይመ። *ፈረሶቻቸውን፤* የ4፥13 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 8፥16 ይመ። *የጽዮን ልጅ፤* ኢየሩሳሌምና ነዋሪዎቿ በሰውኛ ዘይቤ መገለጣቸው ነው (ቍ2፤ 4፥31 ይመ)።

*6፥24-26፤* ነቢዩ ኤርምያስ ለሕዝቡ ይናገራል፤ ስለ ሕዝቡም ይናገራል።

6፥24 *ክንዶቻችንም ዝለዋል፤* ወኔ ከዳቸው ማለት ነው (ኢሳ13፥7 ይመ)። *ጭንቀት፤* የ4፥9 ማብ ይመ።

6፥25 *በየቦታው ሽብር፤* ኤርምያስ ይህን አገላለጽ ስለ ሚወደው በተለያየ ቦታ አስፍሮት ይገኛል (20፥10፤ 46፥5፤ 49፥29)። ለዚህ አባባል የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ "ማጎርሚሳቢብ" መጠሪያ ስም በመሆን ገብቶ ይገኛል (20፥3 ይመ)።

[26]የሕዝቤ ልጅ ሆይ፤ ማቅ ልበሺ፤
በዐመድም ላይ ተንከባለዪ፤
አንድያ ልጁን እንዳጣ ሰው፣
ምርር ብለሽ አልቅሺ፤
አጥፊው በድንገት፣
በላያችን ይመጣልና::

[27]"ብረት እንደሚፈተን፣ የሕዝቤን
መንገድ፣
አካሄዳቸውንም እንድትፈትን፣
አንተን ፈታኝ አድርጌሃለሁ::
[28]ሁሉም ለማማት የሚዞሩ፣
ድድር ዐመፀኞች፣
ናስና ብረት የሆኑ፣
ምግባረ ብልሹዎች ናቸው::
[29]ርሳሱን ለማቅለጥ፣
ወናፉ በብርቱ አናፋ፤
ግን ምን ይሆናል፣ ከንቱ ልፋት ነው፤
ክፉዎች ጠርገው አልወጡምና::
[30]*እግዚአብሔር* ንቆአቸዋልና፣
የተናቀ ብር ተብለው ይጠራሉ::

**ዋጋ ቢስ አምልኮ**

**7** *ከእግዚአብሔር* ወደ ኤርምያስ የመጣው ቃል ይህ ነው፤ [2]"*በእግዚአብሔር* ቤት በር ቁም፤ በዚያም ይህን መልእክት ዐውጅ፤

"'*እግዚአብሔርን* ለማምለክ፣ በእነዚህ በሮች የምትገቡ የይሁዳ ሕዝብ ሁላችሁ፣ *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ:: [3]የእስራኤል አምላክ፣ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "መንገዳችሁንና ሥራችሁን አስተካክሉ፤ እኔም በዚህ ስፍራ እንድትኖሩ አደርጋችኋለሁ:: [4]ይህ '*የእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ፣ *የእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ፣ *የእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ' ነው እያላችሁ በሐሰት ቃል አትታመኑ:: [5]መንገዳችሁንና ሥራችሁን በእርግጥ ብታሳምሩ፣ በመካከላችሁ ቅንነት ቢኖር፣ [6]መጻተኛውንና ድኻ አደጉን፣ መበለቲቱንም ባትጨቍኑ፣ በዚህም ስፍራ ንጹሕ ደም ባታፈሱ፣ የሚጐዷችሁን ሌሎች አማልክት ባትከተሉ፣ [7]ለአባቶቻችሁ ለዘላለም ርስት አድርጌ በሰጠኋቸው ምድር፣ በዚህ ስፍራ አኖራችኋለሁ:: [8]እናንተ ግን፣ ከንቱ በሆኑ የሐሰት ቃላት ታምናችኋል::"

[9]"'ትሰርቃላችሁ፤ ሰው ትገድላላችሁ፤ ታመነዝራላችሁ፤ በሐሰት ትምላላችሁ፤†

6፥26 ዘፍ 21፥16፤ ዘፀ12፥23፤ኢዮ 2፥8፤ ኤር4፥7:8፤9፥1፤18፥22፤ 0፥16፤25፥34:36፤ሕዝ27፥30፤ ዮና 3፥6
6፥27 ኤር 9፥7፤ ዘካ 13፥9
6፥28 ዘሌ19፥16፤ ኤር5፥23፤ሕዝ22፥18
6፥29 ሚል 3፥3
6፥30 መዝ 53፥5፤ 119፥119፤ምሳ17፥3፤ ኤር7፥29፤ሰቆ5፥22፤ ሕዝ22፥18፤ሆሴ9፥17
7፥2 ኤር 17፥19
7፥3 ቍ7፤ኤር18፥11፤26፥13፤35፥15
7፥4 ቍ8፤ኢዮ15፥31፤ኤር28፥15፤ሚክ 3፥11
7፥5 ቍ 3፤ ዘፀ 22፥22፤ዘሌ25፥17፤ ኢሳ1፥17፤ኤር18፥11፤26፥13፤35፥15
7፥6 ዘፀ 20፥3፤ ዘዳ 8፥19፤2ነገ21፥16፤ ኤር 2፥34፤5፥28፤ 19፥4፤ 22፥3፤ ሕዝ 22፥7
7፥7 ዘዳ4፥40፤ ኢሱ 1፥6

6፥26 ***ማቅ ልበሺ፤*** 4፥8 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፍ37፥34 ማብ ይመ:: ***በዐመድ ላይ ተንከባለዪ፤ ... አልቅሺ፤*** ሕዝ27፥30-31 ይመ፤ ከሚክ1፥10 ጋር ያነጻጽሩ:: ***አንድያ ልጁን፤*** ለአባት እጅግ ብርቅዬ የሆነውን ማለት ነው (ዘፍ 22፥12:16፤ አሞ8፥10፤ ዘካ12፥10፤ ሮሜ8፥32 ይመ):: ***አጥፊው፤*** ባቢሎንን ለማለት ነው (የ4፥7 ማብ ይመ)::

*6፥27-30፤* እግዚአብሔር ለኤርምያስ እየተናገረ ነው፤ ብረት አቅላጭ ብረትን እንደሚፈትን፣ ኤርምያስም የይሁዳን ሕዝብ ይፈትን ዘንድ ጌታ ይሾመዋል (9፥7፤ኢሳ1፥25፤ ሚል3፥2-3 ይመ)::

6፥27 ***ብረት እንደሚፈተን፤*** ኢዮ23፥10 ይመ::

6፥28 ***ለማማት የሚዞሩ፤*** በዘሌ19፥16 የተሰጠውን ትእዛዝ በመጣስ ነው:: ***ናስና ብረት፤*** ከወርቅና ከብር ጋር ሲነጻጸሩ ተራ ብረታ ብረት ናቸው:: ***ምግባረ ብልሹዎች ናቸው፤*** ዘዳ31፥29፤ ኢሳ1፥4 ይመ::

*6፥29፤* በጥንት ዘመን፣ ባልነጠረ ብር ላይ እርሳስ ተጨምሮበት የማንጠሩ ሂደት ይካሄድ ነበር:: ብሩንና እርሳሱን የያዘው ከውር እሳት ላይ በተጣደ ጊዜ፣ ከብሩ ጋር የተቀላቀሉትን ለማስወገድ እርሳሱ ከ'ኦክሲጅን' ጋር ይዋሐድና እንደሚያጣብቅ ንጥረ ነገርም ያገለግል ነበር:: እዚህ ላይ ግን የማንጠሩ ሂደት አልተሳካም፤ ምክንያቱ፣ ያልነጠረው ብረታ ብረት ጥራት በቂ አልነበረም (ከሕዝ 24፥11-13 ጋር ያነጻጽሩ)::

6፥30 ***የተናቀ፤*** "የማይመለሱ ዐመፀኞች" (ቍ28)፣ "ክፉዎች" (ቍ29) የእግዚአብሔርን ፈተና ማለፍ አልቻሉም፤ ከእነርሱ ዘንድ የሚበጅ አንዳች ነገር ይገኛል ተብሎ አይታሰብም::

*7፥1-10፥25፤* በዚህ ክፍል የሚገኘው መልእክት ኤርምያስ በተለያየ ጊዜ በቤተ መቅደስ ተገኝቶ ያስተላለፈው ነው፤ ይህም ለብዙ ዓመታት ለሕዝቡ የቀረበ መልእክት ነው:: 26፥2-6:12-15 ላይ ያለው በይዘቱ ከም 7 ጋር ተመሳሳይ ስለ ሆነ፣ ም7-10 (ወይም ቢያንስ ም7) በኢዮአቄም ዘመን የተላለፉ መልእክቶች ሳይሆኑ አይቀርም (26፥1 ይመ):: በሌላም በኩል፣ ብዙውን ፍሬ ሐሳብ ኤርምያስ በረዥሙ የአገልግሎት ጊዜው መላልሶ በመደጋገም አስተላልፎት ሊሆን ይችላል፤ ያም ሆነ ይህ፣ በም 7-10 ካለው ፍሬ ሐሳብ ውስጥ ከንጉሥ ኢዮስያስ ዘመን ጋር የማይስማማ አንድም ጕዳይ የለም::

*7፥1-8፥3፤* በዚህ ክፍል ውስጥ ያለው መልእክት፣ የይሁዳ ሕዝብ ከጣዖት አምልኮ እስካልራቀ ድረስ፣ ቀደም ሲል በሴሎ በነበረው ቤተ መቅደስ ላይ የደረሰው በኢየሩሳሌም በሚገኘው የንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደስም ላይ እንደሚደርስ ይገልጻል::

7፥1 ***የመጣው ቃል፤*** 1፥2 እና ማብ 1፥4:11:13፤2፥1 ይመ::

7፥2 ***በር፤*** በውስጠኛውና በውጭው የቤተ-መቅደሱ ቅጥሮች መካከል የሚገኘው አደባባይ ሲሆን፣ ምናልባትም "አዲሱ በር" ተብሎ የሚጠራው ሊሆን ይችላል (26፥10፤ 36፥10):: ***ስሙ፤*** የ2፥4 ማብ ይመ:: ***ለማምለክ ... የምትገቡ ... ሕዝቦች ሁላችሁ፤*** ምናልባት ሰዎች ከየስፍራው መጥተው ከሚሰበሰቡባቸው ከሦስቱ ዓመት በዓሎች በአንዱ ዕለት ይሆናል (ዘዳ16፥16 እና ማብ ይመ):: ***በሮች፤*** ወደ ውጭው አደባባይ የሚወስዱት ማለት ነው::

7፥3 ***በዚህ ስፍራ፤*** እግዚአብሔር በሰጣቸው ምድር ማለት ነው (ቍ7፤ 14፥13:15፤ 24፥5-6 ይመ):: ***መንገዳችሁንና ... አስተካክሉ፤*** እግዚአብሔር ሕዝቡ ከክፉ መንገዱ እንዲመለስ ዕድል በመስጠት ሌላ ጥሪ ያቀርብላቸዋል፤ ሕዝቡ ግን በቤተ መቅደሱ በመኖርና በውስጡ በሚከናወነው ሥርዐት በመተማመን አንዳች የጐደላቸው ስላልመሰላቸው፣ ንስሓ መግባት አስፈላጊ ሆኖ አልታያቸውም (ቍ4 ይመ)::

7፥4 ***በሐሰት ቃል፤*** በሐሰተኛ ነቢያት የሚነገረው ነው:: የእግዚአብሔር ማደሪያ የሆነው ቤተ መቅደስ በኢየሩሳሌም ስላለ ብቻ፣ ከተማዋ አትጠፋም ብሎ መገመቱ ራስን ማሞኘት ነበር፤ ይህን አጕል መዘናጋት በልባቸው ሊያጕላ የቻለውም በሕዝቅያስ ዘመነ መንግሥት፣ ከተማዋ አንዳች ችግር ሳይደርስበት በታምር መትረፉ በከፊልም ቢሆን አስተዋጽኦ ስላደረገ ነው (2ነገ19፥32-36 ይመ፤ ከ2ሳሙ7፥11-13፤ ከመዝ132፥13-14 ጋር ያነጻጽሩ):: ይሁዳ በእግዚአብሔር ላይ እያደረገች ካለችው ክፉ ዐመፅ አንጻር፣ የዚህ ዐይነቱ አስተሳሰብ "ከንቱ" ነው (ቍ8፤ ሚክ3፥11 ይመ):: ***ይህ ... ነው፤*** ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "እነዚህ ናቸው" የሚል ሲሆን፣ አጠቃላዩን የቤተ መቅደሱንና የተሠራባቸውን የሕንፃ ክፍሎች የሚያመለክት ነው:: ***ቤተ መቅደስ ... ቤተ መቅደስ ... ቤተ መቅደስ፤*** እንዲያው በከንቱ ማነብነብና መደጋገም ማለት ነው (ከማቴ6፥7 ጋር ያነጻጽሩ):: ብዙውን ጊዜ አንድ ቃል ሦስት ጊዜ ሲደገም ለነገሩ የተሰጠውን አጽንዖት የሚያመለክት ነው (22፥29 ይመ፤ የኢሳ6፥3 ማብ በተጨማሪ ይመ)::

*7፥6፤* ገዦችም ሆኑ ሕዝቡ እነዚህን የትንቢት ቃላት ሰምተው በተግባር ሊኖሩባቸው ይገባል (22፥2-3 ይመ):: ***መጻተኛውንና ... ድኻ አደጉን ... መበለቲቱንም፤*** ዘዳ 16፥11:14፤ 24፥19-21፤ 26፥12-13፤ 27፥19 ይመ:: ***ንጹሕ ደም፤*** 19፥4፤ 22፥17፤ 26፥15 ይመ፤ እንዲሁም በአሠቃቂ ድርጊቱ የሚጠቀሰውን የንጉሥ ምናሴን ታሪክ ይመ (2ነገ21፥16)::

7፥7 ***ለዘላለም ... ምድር፤*** ዘፍ17፥8 እና ማብ ይመ::

7፥8 ***የሐሰት ቃላት፤*** የቍ4 ማብ ይመ::

*7፥9፤* በዚህ በአንዱ ጥቅስ ብቻ፣ የዐሥርቱ ቃላት ግማሽ

ለበአል ታጥናላችሁ፤ የማታውቋቸውንም ሌሎች አማልክት ትከተላላችሁ፤ [10]ስሜ ወደ ሚጠራበት ወደዚህ ቤት መጥታችሁ በፊቴ ትቆሙና “ደህና ነን”። እያላችሁ እነዚህን አስጸያፊ ነገሮች ታደርጋላችሁ። [11]ስሜ የሚጠራበት፣ ይህ ቤት በእናንተ ዘንድ የወንበዴዎች ዋሻ ሆኖአልን? እነሆ፤ የምታደርጉትን ነገር አይቻለሁ! ይላል *እግዚአብሔር*።

[12]“ ‘እንግዲህ ቀድሞ የስሜ ማደሪያ አድርጌው ወደ ነበረው ስፍራ ወደ ሴሎ ሂዱ፤ ከሕዝቤ ከእስራኤል ክፋት የተነሣ ያደረግሁበትንም እዩ። [13]እነዚህን ሁሉ ስታደርጉ፣ ይላል *እግዚአብሔር*፣ ደጋግሜ ተናገርኋችሁ፤ እናንተ ግን አላደመጣችሁኝም፤ ጠራኋችሁ፤ እናንተ ግን አልመለሳችሁም። [14]ስለዚህ በሴሎ እንዳደረግሁ አሁንም ስሜ በተጠራበት ቦታ፣ በታመናችሁበት ቤተ መቅደስ፣ ለአባቶቻችሁና ለእናንተ በሰጠሁት በዚህ ስፍራ እንዲሁ አደርጋለሁ፤ [15]ወንድሞቻችሁ የሆኑትን፣ የኤፍሬምን ሁሉ ሕዝብ እንዳስወገድሁ፣ እናንተንም ከፊቴ እጥላችኋለሁ።’

[16]“እንግዲህ ስለማልሰማህ፣ ለዚህ ሕዝብ አትጸልይ፤ ልመና አታቅርብ፤ አትማጠን፤ አትማልድላቸውም። [17]እነርሱ በይሁዳ ከተሞችና በኢየሩሳሌም መንገዶች ላይ የሚያደርጉትን አታይምን? [18]ለሰማይዋ ንግሥት ቂጣ ሊጋግሩ፣ ልጆች እንጨት ይለቅማሉ፤ አባቶች እሳት ያቀጣጥላሉ፤ ሴቶችም ሊጥ ያቦካሉ፤ ሊያስቈጡኝም ለሌሎች አማልክት የመጠጥ ቍርባን ያቀርባሉ። [19]ለመሆኑ ይህን የሚያደርጉት እኔን ለማስቈጣት ነውን? ይላል *እግዚአብሔር*፤ “ይልቁን ይህን በማድረጋቸው በሚደርስባቸው ዕፍረት የሚጐዱት ራሳቸውን አይደለምን?

[20]“ ‘ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ቍጣዬና መዓቴ በዚህ ስፍራ በሰውና በእንስሳ ላይ፣ በዱር ዛፍና በምድር ፍሬ ላይ ይፈሳል፤ ይነዳል፤ አይጠፋም።”

[21]“ ‘የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “የሚቃጠል መሥዋዕታችሁን በሌሎች መሥዋዕታችሁ ላይ ጨምሩ፤ ሥጋውንም ራሳችሁ ብሉ። [22]የቀድሞ አባቶቻችሁን ከግብፅ ባወጣኋቸው ጊዜ፣ ስለ መሥዋዕቶችና ስለሚቃጠል መሥዋዕት አልተናገርኋቸውም፤ ትእዛዝም አልሰጠኋቸውም። [23]ነገር ግን ድምፄን ስሙ፤ እኔም ስምባክ እሆናችኋለሁ፤ እናንተም ሕዝቤ ትሆናላችሁ፤ መልካም እንዲሆንላችሁም፣

7፥8 ቍ4፤ኢዮ 15፥31
7፥9 ዘፀ20፥3:6: 13:14:15፤ዘሌ19፥12፤ዘኍ25፥1፤ኢሳ1፥13፤ኤር11፥13:17፤32፥29፤ ሆሴ2፥13፤ዘካ 8፥17፤ሚል3፥5
7፥10 ቍ 30፤2ነገ 21፥4-5፤ኢሳ48፥1፤ኤር23፥11፤32፥34፤ሕዝ 23፥38-39፤33፥25
7፥11 ዘፍ 31፥50፤መሳ11፥10፤ኢሳ56፥7፤ኤር29፥23፤42፥5፤ማቴ 21፥13፤ማር 11፥17፤ ሉቃ19፥46
7፥12 ዘፀ 40፥2፤ኢሱ18፥1:10፤1ሳሙ 2፥32፤4፥10-11:22፤መዝ78፥60-64፤ዳን 9፥18
7፥13 ቍ26፤2ዜና 36፥15፤መዝ71፥17፤ምሳ1፥24፤ኢሳ48፥17፤65፥12፤ኤር 32፥33፤ 35፥17
7፥14 ቍ4፤መሳ 18፥31፤1ሳሙ2፥32፤1ነገ9፥7፤ሕዝ24፥21
7፥15 ዘፍ 4፥14፤ዘፀ33፥15፤2ነገ17፥20፤መዝ78፥67፤ኤር 23፥39
7፥16 ዘፀ32፥10፤ዘኍ23፥19፤ዘዳ9፥14፤ኤር15፥1
7፥18 ዘዳ31፥17፤1ነገ14፥9፤ኢሳ57፥6፤ኤር44፥17-19 7፥19 ዘዳ32፥21፤ኢዮ7፥20፤ኤር9፥19፤20፥11፤22፥22፤44፥3 7፥20 አዮ40፥11፤ኢሳ1፥31፤30፥15፤ኤር6፥11-12፤11፥16፤13፥14፤15፥6:14፤17፥4:27፤42፥18፤ሰቆ4፥11፤2፥3-5፤ሕዝ20፥47-48 7፥21 1ሳሙ2፥12-17፤ኤር6፥20፤ሆሴ8፥13፤አሞ5፥21-22 7፥22 1ሳሙ15፥22፤ኢሳ43፥23፤ 7፥23 1ዮሐ 3፥23፤ዘፀ19፥5፤ዘሌ26፥12፤ዘዳ5፥33፤1ነገ8፥36፤መዝ119፥3፤ኢሳ 51፥16፤

+9 ወይም *በሐሰተኛ አማልክት ትምላላችሁ*

ተመልክቶአል (ከሆሴ4፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። *ለበአል ታጥናላችሁ፤* የ1፥16 ማብ ይመ። *የማታውቋቸውንም ሌሎች አማልክት ትከተላላችሁ፤* 19፥4 ይመ። ሁኔታቸውና አድራጎታቸው የሚያሳዝን ቢሆንም፣ ይህ ኀጢአት ወደማያውቁት አገር ለመሰደዳቸው ምክንያት ነው (9፥14:16፤ 16፥11:13 ይመ)።

7፥10 *ስሜ ወደሚጠራበት ... ቤት፤* ቍ11:14:30፤ 25፥29፤ 32፥34፤34፥15፤ 1ነገ8፥43፤ 2ዜና6፥33፤20፥9፤ ዳን9፥18 ይመ። እንደዚህ ባሉ ክፍሎች፣ የእግዚአብሔር “ስም” ሲባል እግዚአብሔር ከቸርነቱ የተነሣ ከነሙሉ ክብሩ በዚያ መገኘቱን ያመለክታል (ቍ12:15 ይመ)። *ደህና ነን፤* 12፥12 ይመ። *አስጸያፊ፤* 2፥7 ይመ፤ በተጨማሪም የዘሌ7፥2 ማብ ይመ።

*7፥11፤* ጌታችን ይህን ጥቅስ ከኢሳ56፥7 የመጨረሻ አጋማሽ ጋር በከፊል ጠቅሶታል (ማቴ21፥13፤ ማር11፥17፤ ሉቃ 19፥46)። *የወንበዴዎች ዋሻ፤* ሌቦች ዋሻ ውስጥ ገብተው ሲደበቁ ከሥጋት የሚያመልጡ እንደሚመስላቸው፣ የይሁዳም ሕዝብ የከፋ ኀጢአት ሠርተው ሳለ፣ በቤተ መቅደሱ በከንቱ ይታመናሉ።

*7፥12፤* በ7፥1-8፥3 ባለው ክፍል ላይ የተሰጠውን ማብ ይመ። ... *ስፍራ ... ሴሎ ... ያደረግሁበትንም እዩ፤* ቍ14፤ 26፥6:9፤ መዝ78፥60-61 ይመ። ከነዓን ድል ከሆነች በኋላ የማደሪያው ድንኳን በሴሎ ተተክሎ ነበር (ኢያ18፥1)፤ እስከ ዘመነ መሳፍንት ማብቂያ ድረስም እዚያው ነበር (1ሳሙ1፥9 ይመ)። በአሁኑ ጊዜ ሴሎን በመባል የምትታወቀውና ከኢየሩሳሌም ከተማ ሃያ ዘጠኝ ኪሎ ሜትር ያህል በስተ ሰሜን ርቆ በሚገኘው የባቡር ሐዲድ አጠገብ የምትገኘው የጥንቱን ቦታ ስም ይዛ ትገኛለች። የሥነ ቅርስ ቍፋሮ ውጤት እንደሚጠቍመው ይህች ከተማ በ1050 ዓ.ቅ.ክ አካባቢ በፍልስጥኤማውያን እጅ ጠፍታለች። የማደሪያው ድንኳን ግን በዚህ ጊዜ አብሮ እንዳልወደመ ይታወቃል፤ ምክንያቱም በዳዊት ዘመነ መንግሥት በገባዖን ይገኝ እንደ ነበረ ተጠቅሶአል (1ዜና21፥29)። ሕዝቡ በዚያ ከሚፈጽመው የአምልኮ ሥርዐት ጋር በተያያዘ ሁኔታ፣ አንድ ወይም ከዚያ በላይ የሚሆኑ ቤቶች በሴሎ በነበረው የማደሪያ ድንኳን አጠገብ ተሠርተው እንደ ነበር ይገመታል (በ1ሳሙ3፥15 “የእግዚአብሔር ቤት በሮች” ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ)። እነዚህ ሕንጻዎች ምናልባት በ1ሳሙ4 ላይ በተመለከተው ውድመት፣ ከከተማዋ ጋር አብረው ሳይወድሙ አልቀረም።

7፥13 *ደጋግሜ፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በትንቢተ ኤርምያስ ውስጥ በብዙ ቦታ ተጠቅሶ ይገኛል (ቍ25፤11፥7፤25፥3-4፤26፥5፤ 29፥19፤32፥33፤ 35፥14-15፤ 44፥4)፤ ይሁን እንጂ በብሉይ ኪዳን ውስጥ ሌላ ስፍራ አይገኝም።

7፥15 *ከፊቴ እጥላችኋለሁ፤* በምርኮኝነት እንዲሰደድ ነው (ዘዳ29፥28 ይመ)። *ወንድሞቻችሁ የሆኑትን ... ሁሉ እንዳስወገድሁ፤* እግዚአብሔር የሰሜኑን ክፍል መንግሥት፣ እስራኤልን በ721 ዓ.ቅ.ክ. በምርኮ እንዲጋዙ አድርጎአቸዋል (2ነገ 17፥20 ይመ)። *ኤፍሬም፤* ለእስራኤል የተሰጠ ሌላ ስም ነው (ለምሳሌ:- 31፥9 ይመ)፤ በሌላ አነጋገር፣ ሴሎ የሚገኝበትን የነገድ ክልል በምፀት መልክ ለማመልከት የተነገረ አባባል ነው።

*7፥16፤* በም26 ላይ የሚገኘው ሁኔታ ምናልባት ተገቢ የቅደም ተከተል ቦታው በቍ15 እና በቍ16 መካከል ሊሆን ይችላል። *ለዚህ ሕዝብ አትጸልይ፤* እውነተኛ ነቢይ ማድረግ እንደሚገባው ማለት ነው (27፥18፤ ዘፀ32፥31-32፤ 1ሳሙ12፥23 ይመ)። 11፥14፤ 14፥11 ይመ። ለሕዝቡ የቀረለት ተስፋ ያለ አይመስልም። ይሁን እንጂ ኤርምያስ በተለያየ ጊዜ ለወገኖች ጸልዮአል (ለምሳሌ:- 18፥20 ይመ)።

7፥18 *ልጆች ... አባቶች ... ሴቶችም፤* ቤተ ሰቡ ሁሉ በጣዖት አምልኮ ሥርዐት ተካፋይ ነበር ማለት ነው። *ቂጣ፤* 44፥19 ይመ። *ለሰማይዋ ንግሥት፤* አስታሮት ለተባለችው ጣዖት ባቢሎናውያን የሰጧት መጠሪያ ነበር፤ እርሷም በሁለ ገቡ የባቢሎን ቤተ ጣዖታት ውስጥ ትልቅ ስፍራ ነበራት። *ለሌሎች አማልክት የመጠጥ ቍርባን፤* አንዳንድ ጊዜ ሳራሷ ለሰማይዋ ንግሥትም ያቀርቡ ነበር (44፥19:25 ይመ)። *ሊያስቈጡኝም፤* ዘዳ31፥29 ይመ።

7፥19 *በሚደርስባቸው ዕፍረት፤* 3፥25 ይመ።

*7፥20፤* እግዚአብሔር በኃጥአን ላይ ቍጣውን በሚያወርድበት ጊዜ፣ ፍጥረታት ሁሉ በአንድ ላይ መከራ ይደርስባቸዋል (5፥17፤ ሮሜ8፥20-22 ይመ)። *ይነዳል፤ አይጠፋም፤* 4፥4፤ 21፥12 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ1፥31፤ አሞ 5፥6 ይመ።

*7፥21፤* ከክፉ ተግባራችሁ የተነሣ፣ የምታቀርቡት መሥዋዕት ሁሉ ተቀባይነት ስለሌለው እናንተው ብሉት ማለት ነው።

*7፥22-23፤* መሥዋዕት ተቀባይነት የሚኖረው፣ ከልብ የሆነ ንስሓና ቅንነት የተሞላበት መታዘዝ አብሮ ሲገኝ ነው (6፥20፤ ኢሳ1፥11-15 እና ማብ ይመ)።

7፥23 *እኔም ... እሆናችኋለሁ፤ ... ሕዝቤ ትሆናላችሁ፤*

ባዘዝኋችሁ መንገድ ሁሉ ሂዱ ብዬ አዘዝ ኋቸው:: [24]እነርሱ ግን አልሰሙም፤ ልብ ብለው ለማድመጥም አልፈለጉም፤ ይልቁን የክፉ ልባቸውን ሐሳብ በእልኸኝነት ተከ ተሉ፤ ወደ ፊት በመሄድ ፈንታም ወደ ኋላቸው ተመለሱ:: [25]አባቶቻችሁ ከግብፅ ምድር ከወጡበት ጊዜ ጀምሮ እስካሁን ድረስ፣ በየቀኑ ሳላሰልስ አገልጋዮቼን ነቢ ያትን ላክሁባቸው:: [26]ሕዝቡ ግን አልሰማ ኝም፤ ልብ ብሎ ለማድመጥም አልፈለገም፤ ዐን ገታቸውን አደነደኑ አባቶቻቸው ከሠሩት የባ ሰም ክፉ አደረጉ::" '

[27]"ይህን ሁሉ ትነግራቸዋለህ፤ እነርሱ ግን አይሰሙህም፤ ትጠራቸውማለህ፤ አይመልሱ ልህም:: [28]ስለዚህ እንዲህ በላቸው፤ 'ይህ ሕዝብ ለአምላኩን *እግዚአብሔርን* ያልታዘዘ፣ ምክሩን ያልተቀበለ ወገን ነው፤ እውነት ጠፍ ቶአል፤ ከአንደበታቸውም ሸሽቶአል:: [29]*እግዚ አብሔር* ቍጣው የወረደበትን ይህን ትው ልድ ስለ ናቀውና ስለ ተወው፣ ጠጕርሽን ቈርጠሽ ጣይ፤ በባድሞቹ ኮረብቶች ላይ ሆነሽም ሙሾ አውጪ::

## የዕርድ ሸለቆ

[30]" 'የይሁዳ ሕዝብ በፊቴ ክፉ ነገር አድ ርጓል፤ ይላል *እግዚአብሔር*፤ አስጸያፊ ነገራ ቸውን ስሜ በተጠራበት ቤት በማስቀ መጥ አርክሰውታል:: [31]እኔ ያላዘዝኋቸውን፣ ከቶም ያላሰብሁትን ወንዶችና ሴቶች ልጆ ቻቸውን በእሳት አቃጥለው ለመሠዋት በሄኖም ልጅ ሸለቆ የቶፌትን መስገጃ ኮረ ብቶች ሠሩ:: [32]ስለዚህ አስተውሉ፤ ይላል *እግዚአብሔር*፤ ስፍራ እስከማይገኝ ድረስ ሙታንን በቶፌት ስለሚቀብሩ፣ የዕርድ ሸለቆ እንጂ ከእንግዲህ ቶፌት ወይም የሄ ኖም ልጅ ሸለቆ ተብሎ የማይጠራበት ጊዜ ይመጣል::

[33]የዚህም ሕዝብ ሬሳ ለሰማይ ወፎችና ለምድር አራዊት ሲሳይ ይሆናል፤ የሚያባር ራቸውም አይኖርም:: [34]የደስታና የተድላን ድምፅ፣ የሙሽራና የሙሽራዪቱን ድምፅ ከይሁዳ ከተሞችና ከኢየሩሳሌም መንገዶች አጠፋለሁ፤ ምድሪቱ ባድማ ትሆናለችና::

**8** " 'በዚያን ጊዜ፣ ይላል እግዚአብሔር፤ የይሁዳን ነገሥታትና መኳንንት ዐፅም፣ የካህናትና የነቢያት ዐፅም፣ የኢየሩሳሌም

7፥24 ኤር6፥10፤ 11፥8፤17፥23፤34፥14፤3፥17፤2፥19፤ሕዝ 37፥23
7፥25 ዘኍ11፥29፤ 2ዜና36፥15፤ኢሳ20፥3፤ኤር25፥4፤35፥15
7፥26 ቍ 13:24፤ ዘፀ32፥9፤2ዜና36፥16፤ መዝ81፥11፤ኤር13፥11፤16፥12፤22፥21፤ 25፥3፤35፥15፤ሕዝ 20፥8:21፤ሚል3፥7፤ ሉቃ11፥47፤ሐሥ 7፥51
7፥27 ቍ 13፤ኢሳ 65፥12፤ሕዝ2፥7፤ 3፥7፤ዘካ7፥13
7፥28 ዘሌ 26፥23፤ መዝ15፥2፤ኢሳ59፥15፤ሶፎ3፥7
7፥29 ዘሌ 21፥5፤ ኢዮ1፥20፤ኤር4፥8፤ 6፥30፤12፥7፤ሕዝ19፥1፤ሆሴ11፥8፤ሚክ5፥3
7፥30 ቍ10፤ ዘሌ 18፥21፤20፥3፤ኤር 2፥7፤4፥1፤32፥34፤ሕዝ 7፥20-22፤
7፥31 ዘሌ18፥21፤ ኢሱ15፥8፤2ነገ23፥10፤2ዜና33፥6፤ኤር19፥5 32፥35፤ሕዝ16፥20፤ 20፥31፤ሚክ6፥7
7፥32 ኤር19፥6:11 7፥33 ዘፍ15፥11፤ዘዳ28፥26፤ኤር6፥11፤ 14፥16፤ሕዝ29፥5 7፥34 ዘሌ26፥34፤ኢሳ24፥7-12:8፤ኤር33፥10፤ ዘካ7፥14፤ማቴ23፥38፤ራእ18፥23 8፥1 መዝ53፥5፤ኢሳ14፥19

በሲና ተራራ ላይ በተደረገው ኪዳን፣ እውን የሆነውን የእግዚ አብሔርንና የእስራኤልን ግንኙነት በአጭሩ የሚገልጽ መሠረታዊ አባባል ነው (ዘፀ6፥7፤ዘሌ26፥12 እና ማብ፤ ዘዳ26፥17-18 ይመ)::

7፥24 *የክፉ ልባቸውን ... ተከተሉ*፤ የ3፥17 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዘፍ6፥5 እና ማብ ይመ::

7፥25 *በየቀኑ ሳላሰልስ*፤ የቍ13 ማብ ይመ:: *አገልጋዮቼን ነቢያትን*፤ 25፥4፤ 26፥5፤ 29፥19፤ 35፥15፤ 44፥4 ይመ፤ እንዲ ሁም ዘካ1፥6 እና ማብ ይመ:: በጌታ ስም ከሚናገሩትና በታ ማኝነት ከሚያገለግሉት ብዙ ነቢያት መካከል ሙሴ የመጀ መሪያው እንደሚሆን እግዚአብሔር ቃል ገብቶለታል (ዘዳ18፥15-22 እና ማብ ይመ)::

7፥26 *አንገታቸውን አደነደኑ*፤ 17፥23፤ 19፥15 ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ32፥9፤ ነህ3፥5 ማብ ይመ::

7፥28 *ምክሩን ያልተቀበለ*፤ 2፥30፤ 5፥3 ይመ:: *እውነት ... ከአንደበታቸውም ሸሽቶአል*፤ እውነትን የሚፈልግ አንድም ሰው የለም (5፥1 እና ማብ ይመ)::

*7፥29*፤ ለኢየሩሳሌም ለራሷ የተነገረ ነው:: *ጠጕርሽን ቍርጠሽ*፤ የሐዘን ምልክት ነው (ኢዮ1፥20፤ ሚክ1፥16 ይመ):: "ጠጕር" ለሚለው የገባው የዕብራይስጡ ቃል "ናዝራዊ" ከሚ ለው ቃል ጋር ይዛመዳል (ዘኍ6፥2 ይመ)፤ ከአመጣጡ የሚያመ ለክተውም ሊቀ ካህናቱ ራሱ ላይ የሚደፋውን አክሊል ነበር (ዘፀ 29፥6 ይመ):: የናዝራዊ ጠጕር የመለየቱና የመቀደሱ ምልክት ነበር (ዘኍ6፥7):: ናዝራዊው የታዘዘውን ሥርዐት መጠበቅ ተስ ኖት ቢረክስ፣ ጠጕሩን እንዲቈረጥ እንደታዘዘ ሁሉ (ዘኍ6፥9)፣ ኢየሩሳሌምም በኀጢአቷ ምክንያት ጠጕሯን መላጨት ይገ ባታል:: *በባድሞቹ ኮረብቶች ላይ ሆነሽም ሙሾ አውጪ*፤ 3፥21 ይመ፤ እንዲሁም የ3፥2 ማብ ይመ::

7፥30 *አስጸያፊ ነገራቸውን ... ቤት በማስቀመጥ*፤ ምናሴ በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ውስጥ የተቀረጸውን የአሼራ ምስል አስቀምጦ ነበር (2ነገ21፥7):: በኤርምያስ ዘመን የነበረው ደግ ንጉሥ ኢዮስያስ ግን የጣዖት ምስሎችንና ሌሎችን የጣዖት ማምለኪያ ዕቃዎች አስወግዶ ነበር (2ነገ23፥4-7):: ነገር ግን ኢዮ ስያስ ከሞተ በኋላ ሃያ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ አያሌ የጣዖት ምስሎች በቤተ መቅደሱ አደባባይ ውስጥ እንደ ነበሩ ሕዝ ቅኤል አመልክቶአል (ሕዝ8፥3:5:6:10:12 ይመ):: *አርክሰውታል*፤ የ2፥7 ማብ ይመ::

7፥31 *መስገጃ ኮረብቶች*፤ የአረማውያንን የአምልኮ ማእ ከል የሚያመለክቱ ናቸው፣ ብዙውን ጊዜ (እዚህ ላይ ግን አይደለም) በተፈጥሮ ጕብ ብለው በሚገኙ ቦታዎች ላይ ይሠሩ ነበር (1ሳሙ9፥13-14፤ 10፥5፤ 1ነገ11፥7 ይመ):: *ቶፌት*፤ ቍ32፤ 19፥6:11-14 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ30፥33 ማብ ይመ:: ቃሉ ከአራማይክ (ዕብራይስጥ) ሳይመጣ አይቀርም፤ ትርጕሙም፤ "ምድጃ" ማለት ነው፤ ይሁን እንጂ ከእስራኤል ባህል ውጭ በሆነው ዓለም ዘንድ የወል ስም በመሆን፣ "የሕፃናት መሠዊያ ቦታ" የሚል ትርጕም ተሰጥቶታል:: ቃሉ ባለው የአገባብ ድምፅ ሆን ተብሎ ከዕብራይስጡ "ቦሼት" ጋር እንዲቀራረብ የተደረገ ይመስላል፤ "ቦሼት"፣ "አሳፋሪ ነገር" ማለት ነው (የመሳ6፥32 ማብ ይመ)፤ ይህ አባባል በአገባብ ውስጥ ውሉ የሚገኘው በአብዛኛው ከባዕድ አምልኮ ጋር ተያይዞ ነው (የ2፥26፤ 3፥25 ማብ ይመ):: የብሉይ ኪዳኑ ቶፌት እሳት ማንደጃ ጕድጓድ ነበረው (ኢሳ30፥33 ይመ)፤ ያልታደሉ ምስኪን ሕፃናትም ወደ ዚያ ይጣሉ ነበር:: *በሄኖም ልጅ ሸለቆ*፤ ቍ32፤ 19፥2:6፤ 32፥35 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሱ 15፥5 ማብ ይመ:: ይህ ሸለቆ የአካባቢው ቈሻሻ መጣያ ከመሆኑም በላይ ሕፃናት ለባዕድ አማ ልክት የሚሠዉበት ቦታ ነበር:: "የሄኖም ሸለቆ" ከሚለው (ነህ11፥30 ይመ) የዕብራይስጡ አጭር አጠራር (ገ-ሄኖም) በአዲስ ኪዳን ውስጥ በክርስቶስ ያላመኑ ሰዎች ለዘላለም በእሳት የሚቃጠሉበትን የፍርድ መፈጸሚያ ስፍራ የሚያመለክተው "ገሃነም" የሚለው ቃል ተገኝቶአል (ለምሳሌ:- ማቴ18፥9፤ ማር 9፥47-48 ይመ):: *ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን በእሳት አቃጥለው*፤ በአሠቃቂ ተግባር የተሞላ የሃይማኖት ሥርዐት ሲሆን፣ በሙሴ ሕግ የተከለከለ ነበር (ዘሌ18፥21 እና ማብ፤ ዘዳ18፥10 ይመ)፤ ይሁን እንጂ አካዝ (2ነገ16፥2-3 ይመ) እንዲሁም ምናሴ (2ነገ21፥1:6) ይህንኑ ተግባር ፈጽመዋል::

7፥32 *ስለዚህ አስተውሉ ... የዕርድ ሸለቆ*፤ ይህ አባባል በ19፥6 ላይ ከብዙ በጥቂቱ እንዳለ ተደግሞአል:: ወራሪዎቹ ባቢ ሎናውያን በሚመጡበት ጊዜ የይሁዳን ሕዝብ ስለሚ ያርዷቸው፣ መሠዊያ ቦታ አድርገውት የነበረው ይህ ሸለቆ መቀበሪያቸው ይሆናል::

*7፥33*፤ እዚህ ላይ የተገለጸው ቅጣት ኪዳኑን ማፍረስ ከሚያስከትለው እርግማን አንዱ ነው (ዘዳ28፥26 ይመ):: *ለሰማይ ወፎች ... ሲሳይ*፤ 16፥4፤ 19፥7 ይመ፤ በተጨማሪም የእግዚ አብሔርን ኪዳን ባለመጠበቅ ተመሳሳይ ፍርድ የተጠቀሰበትን (34፥18-19) 34፥20 ይመ:: ሬሳ ሳይቀበር መንገድ ላይ ቀረ ማለት በጥንት ዘመን እጅግ አስነዋሪ ጉዳይ ነበር::

*7፥34*፤ 16፥9፤ 25፥10 ይመ፤ ከ33፥10-11 ጋር ያገናዝቡ:: *ምድሪቱ ባድማ ትሆናለች*፤ የእግዚአብሔርን ኪዳን ካለመጠበቅ የተነሣ የሚወርድ ሌላኛው እርግማን ነው (ዘሌ26፥31:33)::

8፥1 *ዐፅም ... ከየመቃብሩ ይወጣል*፤ ትልቅ ውርደትና ቅሌት ነበር (2ነገ23፥16:18፤ አሞ2፥1 እና ማብ ይመ):: *ነገሥ*

ሕዝብ ዐፅም ከየመቃብራቸው ይወጣል። [2]በወደዷቸውና በአገለገሏቸው እንዲሁም በተከተሏቸው፣ ባማከሯቸውና ባመለኳቸው በፀሓይ፣ በጨረቃና በሰማያት ከዋክብት ሁሉ ፊት ይሰጣል፤ አይሰበሰብም ወይም አይቀበርም፤ ነገር ግን እንደ ተጣለ ጕድፍ በምድር ላይ ይበተናል። [3]ከዚህ ክፉ ሕዝብ የተረፉት ሁሉ፣ ባሳደድኋቸው ስፍራ ሁሉ ከሕይወት ይልቅ ሞትን ይመርጣሉ፤ ይላል የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር*።'

## ኀጢአትና ያስከተለው ቅጣት

[4]"እንዲህ በላቸው፤ '*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

"'ሰዎች ቢውድቁ፣ እንደገና ከወደቁበት
አይነሡምን?
ሰው ተሳስቶ ወደኋላ ቢሄድ፣ ከስሕተቱ
አይመለስምን?
[5]ታዲያ፣ ይህ ሕዝብ ለምን ፊቱን አዙሮ
ወደ ኋላ ይሄዳል?
ለምንስ ኢየሩሳሌም ዘወትር ወደ ኋላ
ትመለሳለች?
ተንኰልን የሙጥኝ ብለው ይዘዋል፤
ሊመለሱም ፈቃደኛ አይደሉም።
[6]እኔ በጥንቃቄ አደመጥኋቸው፤
ትክክለኛ የሆነውን ግን አይናገሩም።
ማንም ስለ ክፋቱ ንስሓ የገባ የለም፤
"ምን አድርጌአለሁ?" ይላል።
ለጦርነት እንደ ተዘጋጀ ፈረስ፣
እያንዳንዱ በራሱ መንገድ ይሄዳል።
[7]ሽመላ እንኳ በሰማይ፣
የተወሰነ ጊዜዋን ታውቃለች፣
ዋኖስ፣ ጨረባና ዋርዳም፣
የሚሰደዱበትን ጊዜ ያውቃሉ፤
ሕዝቤ ግን፣
*የእግዚአብሔርን ሥርዐት* አላወቀም።
[8]"'የጸሓፊዎቻችሁ ሐሰተኛ ብርዕ ሐሰት
እያስተናገደ እንዴት፣ "ዐዋቂዎች ነን፣
*የእግዚአብሔር ሕግ* አለን" ትላላችሁ?
[9]ጥበበኞች ያፍራሉ፤
ይዋረዳሉ፤ በወጥመድም ይያዛሉ።
*የእግዚአብሔርን ቃል* ተቃውመው፣
ምን ዐይነት ጥበብ ይኖራቸዋል?
[10]ስለዚህ ሚስቶቻቸውንም ለሌሎች
ወንዶች እሰጣለሁ፤
ዕርሻዎቻቸውንም ለባዕዳን እሰጣለሁ፤
ከታናሹ እስከ ታላቁ ድረስ፣
ሁሉም ተገቢ ላልሆነ ጥቅም ይስገበገባሉ፤
ነቢያትና ካህናትም እንዲሁ፤
ሁሉም ያጭበረብራሉ።
[11]የሕዝቤን ቍስል ብርቱ እንዳይደለ
በመቍጠር፣
የተሚላ ፈውስ ሳይኖር እንዲሁ
ያክማሉ፤
ሰላም ሳይኖር፣
"ሰላም፣ ሰላም" ይላሉ።
[12]ርኵሰት ሲፈጽሙ ዐፍረው ነበርን?
የለም! በጭራሽ አላፈሩም፤
ኀፍረት ምን እንደሆነም አያውቁም።
ስለዚህ ከወደቁት ጋር ይወድቃሉ፤
በምቀጣቸው ጊዜ ይዋረዳሉ፤"
ይላል *እግዚአብሔር*።
[13]"'*የመረቱትን* ሁሉ እወስድባቸዋለሁ፤
ይላል *እግዚአብሔር*፤
በወይን ተክል ላይ የወይን ፍሬ አይኖርም፤

8፥2 2ነገ 9፥37፤ 23፥5፤ኢዮ31፥27፤ ኤር14፥16፤19፥13፤ 31፥40፤36፥30፤ሕዝ 29፥5፤37፥1፤ሶፎ1፥5፤ ሐሥ7፥42
8፥3 ዘዳ 29፥28፤ ኢዮ3፥22፤ራእ 9፥6
8፥4 መዝ119፥67፤ ምሳ24፥16፤ኤር31፥19፤ሚክ7፥8
8፥5 ኤር5፥27፤ዘካ 7፥11
8፥6 መዝ 14፥1-3፤ ሚል3፥16፤ራእ9፥20
8፥7 ዘዳ 32፥28፤ ኤር4፥22
8፥8 ሮሜ 2፥17
8፥9 2ነገ 19፥26፤ ኢዮ5፥13፤ምሳ1፥7፤ ኢሳ29፥14፤ኤር6፥19 ፤1ቆሮ1፥20
8፥10 ኢሳ 56፥11፤ ኤር6፥12፤14፥14፤ ኤር23፥11፡15፤ ሰቆ 2፥14
8፥11 ቍ 15፤ ኤር 4፥10፤ሕዝ7፥25
8፥12 መዝ52፥5-7፤ ኢሳ3፥9፤ኤር 3፥3፤ 6፥15
8፥13 ኤር 5፥17፤ ሆሴ2፥12፤ኢል1፥7፤ ማቴ21፥19፤ሉቃ 13፥6

---

*ታትና መኳንንት፣ ካህናትና ነቢያት*፤ 2፥26 ይመ፤ እንዲሁም የ1፥18 ማብ ይመ።

8፥2 *በፀሓይ፣ በጨረቃና በሰማያት ከዋክብት ... ይሰጣል*፤ የአካላቱን መፈራረስ ለማፋጠንና ምናልባትም፣ ከብዙ ጥቂቱን ለመጥቀስ፣ እንዳንድ የይሁዳ ነገሥታት ያመለኳቸው ሰማያውያን አካላት (2ነገ21፥3:5፤ 23፥11 ይመ) ምንም ሊረዷቸው እንዳልቻሉ ለማሳየት ይሆናል። *በወደዷቸውና ባገለገሏቸው፣ በተከተሏቸውና ባማከሯቸው ... ባመለኳቸው*፤ ይህ ሁሉ ዝቅ ብሎ ማደር ለእግዚአብሔር ብቻ የሚገባ ነበር። *አይሰበሰብም፤ አይቀበርም*፤ ከ2ሳሙ21፥13-14 ጋር ያገናዝቡ። *ጕድፍ*፤ የዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም "ፍግ" ማለት ነው (9፥22፤ 16፥4፤ 25፥33 ይመ)።

8፥3 *የተረፉት*፤ የ6፥9 ማብ ይመ።

*8፥4-9፥26*፤ በ7፥1-8፥3 ከሚገኘው ክፍል ጋር ሲነጻጸር፣ ይህ ክፍል ባብዛኛው በግጥም መልክ የቀረበ ነው። ኤርምያስ በኀጢአተኞች ላይ የሚመጣው፣ መለኮታዊ ፍርድ የማይቀር መሆኑን በማሳየት ገለጻውን ይቀጥላል።

8፥4 ... *በላቸው*፤ ይህን ክፍል ከቀድሞው ክፍል (7፥28 ይመ) ጋር የሚያገናኝ ነው። *ተሳስቶ ወደ ኋላ ቢሄድ፣ ... አይመለስምን?* በዕብራይስጡ "መሳት" ለሚለውና "መመለስ" ለሚለው የገባው ቃል ተመሳሳይ በመሆኑ በሥነ ጽሑፍ ውስጥ የቃላት ጨዋታ እንዳለ ያመለክታል።

*8፥5*፤ በቍ4 ላይ የተጠቀሰውን አጠቃላይ እውነታ እዚህ ላይ የኢየሩሳሌም ሕዝብ ዘወትር ሆን ብለው ሲጥሱት ይታያሉ። *ፊቱን አዙሮ ... ወደ ኋላ ትመለሳለች ... ሊመለሱም*፤ እነዚህ ሦስቱ ቃላት ልክ ቍ4 ላይ እንዳለው ተመሳሳይነት ስላላቸው በዕብራይስጡ የቃላት ጨዋታ ይታይባቸዋል።

8፥6 *እኔ*፤ እግዚአብሔር ማለት ነው። *ይሄዳል*፤ ለዚህ የገባው ዕብራይስጡ በቍ4-5 ያለውን የቃላት ጨዋታ የሚቀጥል ነው። *በራሱ መንገድ*፤ ይህም ወደ ክፋት የሚያመራ ነው (23፥10 ይመ)።

*8፥7*፤ ኢሳ1፥3 ይመ። ከስፍራ ስፍራ የሚጓዙ ወፎች እግዚአብሔር በውስጣቸው ያስቀመጠውን ተፈጥሮአዊ ዕውቀት በመጠቀም እንደ ሁኔታው በመታዘዝ ይኖራሉ፤ ዐመፀኞቹ የእግዚአብሔር ሕዝብ ግን የእግዚአብሔርን ሕግ አይታዘዙም። *ጨረባና ዋርዳም*፤ እነዚህ ሁለቱ በኢሳ38፥14 ላይም በአንድ ላይ ቀርበው ይገኛሉ። *የእግዚአብሔርን ሥርዐት አላወቀም*፤ የ5፥4 ማብ ይመ።

8፥8-9 *የእግዚአብሔር ሕግ ... የእግዚአብሔርን ቃል*፤ የመጀመሪያውን (የተጻፈውን የሙሴ ሕግ) በትክክል ሳያብራሩ ወደ ተፈለገው መንገድ ማመቻቸት፣ ሁለተኛውን (በአገልጋዮቹ በነቢያት የተነገረውና በሕጉ ውስጥ የሚገኘውን የእግዚአብሔርን እውነት) ወደ መናቅና መተው ያደርሳል።

8፥8 *ሐሰተኛ ... ብርዕ*፤ ተጽፎ የሚገኘውን ሕግ እንዳመቻቸው መተርጐማቸውንና መተግበራቸውን የሚያመለክት ተምሳሌት ነው። *የጸሓፊዎቻችሁ*፤ ይህ ቡድን ታዋቂ እንደ ነበረ የሚያሳይ እጅግ ጥንታዊ ፍንጭ ነው። እነዚህ ጸሐፍት (ወይም ጸሓፊዎች የተባሉት) በቤተ ዘመድ ላይ በተመሠረተ ግንኙነት የተደራጁ ይመስላሉ (1ዜና2፥55፤ 2ዜና34፥13 ይመ)። *እንዲዛባ*፤ ከ2ጢሞ2፥15 ጋር ያገናዝቡ።

8፥9 *ተቃውመው ... ጥበብ*፤ ከዘዳ4፥5-6 ጋር ያገናዝቡ።

*8፥10-12*፤ 6፥12-15 እና ማብ ይመ።

*8፥13-9፥24*፤ ይህ ክፍል በየዓመቱ፣ "አቢብ" በተባለው ወር በዘጠነኛው ቀን ሁልጊዜ ድምፅን በማጕላት በምኵራብ ይነበባል፤ ይህ ዕለት በኢየሩሳሌም የነበረው ቤተ መቅደስ በ586 ዓ.ቅ.ክ በባቢሎናውያን፣ በ70 ዓ.ም ደግሞ በሮማውያን እጅ የወደመበት ቀን ነው።

8፥13 *በወይን ተክል*፤ እስራኤልን የሚያመለክት ነው

በበለስ ዛፍ ላይ የበለስ ፍሬ አይገኝም፤
ቅጠሎቻቸውም ይረግፋሉ::
የሰጠኋቸው በሙሉ፣
ከእነርሱ ይወሰድባቸዋል::[ቸ] ”

14“ለምን እዚህ እንቀመጣለን?
በአንድነት ተሰብሰቡ!
ወደ ተመሸጉት ከተሞች እንሽሽ፤
በዚያም እንጥፋ!
በእርሱ ላይ ኀጢአትን ስላደረግን፣
*እግዚአብሔር* አምላካችን እንድንጠፋ
አድርጎናል፤
የተመረዘ ውሃ እንድንጠጣ ሰጥቶናል::
15ሰላምን ተስፋ አደረግን፤
መልካም ነገር ግን አልመጣም፤
የፈውስ ጊዜን ተመኘን፤
ነገር ግን ሽብር ብቻ ሆነብን::
16የጠላት ፈረሶች ፉርፉርታ፣
ከዳን ይሰማል፤
በድንጕላ ፈረሶቻቸው ማሽካካት፣
መላዋ ምድር ተንቀጠቀጠች::
ምድሪቱንና በውስጧ ያለውን ሁሉ፣
ከተማዪቱንና በውስጧ የሚኖሩትን
ሁሉ፣
ሊውጡ መጡ::”

17“እነሆ፤ በመካከላችሁ መርዘኛ እባቦችን፣
የአስማተኛ ብልኀት የማይገታቸው
እፉኝቶችን እሰዳለሁ፤
እነርሱም ይነድፉአችኋል፤”
ይላል *እግዚአብሔር*::
18በሐዘኔ የምታጽናናኝ[ኀ] ሆይ፤
ልቤ በውስጤ ዝላለች::

19እንዲህ የሚለውን የሕዝቤን ጩኸት፣
ከሩቅ ምድር ስማ:-
*እግዚአብሔር* በጽዮን የለምን?
ንጉሥዋስ በዚያ አይኖርምን?”
“በተቀረጹ ምስሎቻቸው፣
እንዲሁም ከንቱ በሆኑ ባዕዳን ለምን
አስቈጡኝ?”

20“መከሩ ዐለፈ፤
በጋው አበቃ፤
እኛም አልዳንም::”

21ሕዝቤ ሲቈስል፣
እኔም ቈሰልሁ፤
አለቀስሁ፤ ድንጋጤ ያዘኝ::
22በገለዓድ የሚቀባ መድኀኒት የለምን?
ወይስ በዚያ ሐኪም አልነበረምን?
ለሕዝቤ ቍስል፣
ለምን ፈውስ አልተገኘም?

9 ስለታረዱት ወገኖቼ፣
ቀንና ሌሊት አለቅስ ዘንድ፣
ምነው፣ ራሴ የውሃ ምንጭ በሆነ!
ምነው ዐይኖቼ የእንባ መጕረፊያ
በሆኑልኝ!
2ሕዝቤን ትቼ፣ ርቄ እንድሄድ፣
በምድረ በዳ የእንግዶች ማደሪያ ማን
በሰጠኝ!
ሁሉም አመንዝሮች፣
የአታላዮች መንጋ ሆነዋላ!

8፥14 ዘዳ 29፥18፤ ኢሱ10፥20፤ኤር9፥15፤14፥7፡20፤23፥15፤ 35፥11፤ዳን9፥5
8፥15 ቍ11፤ኢዮ 19፥8፤ኤር14፥19
8፥16 ዘፍ30፥6፤ኤር 4፥29፤5፥17፤51፥29
8፥17 ዘኍ21፥6፤ ዘዳ32፥24፤መዝ58፥5፤ ኢሳ3፥3
8፥18 ሰቆ 5፥17
8፥19 ዘዳ 28፥64፤ 32፥21፤ኢሳ41፥24፤ ኤር9፥16፤44፥3፤ሚክ 4፥9
8፥21 መዝ94፥5፤ 78፥40፤ኢሳ43፥24፤ ኤር4፥19፤10፥19፤ 14፥17፤30፥14፤ሰቆ 2፥13፤ሕዝ6፥9
8፥22 ዘፍ37፥25፤ ኢዮ13፥4፤ኢሳ1፥6፤ ኤር30፥12
9፥1 መዝ119፥136፤ ኢሳ22፥4፤ኤር13፥17 ፤14፥17፤ሰቆ2፥11፡ 18፤3፥48
9፥2 ዘኍ 25፥1፤ 1ነገ19፥10፤መዝ55፥7 ፤ኢሳ24፥16፤ኤር23፥ 10፤ሆሴ4፥2፤7፥4

[ቸ]13 በዕብራይስጡ የዚህ ስንኝ/ ዐ/ነገር ትርጕም በግልጽ አይ ታወቅም
[ኀ]18 *የምታጽናናኝ* በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጕም በግልጽ አይ ታወቅም

(2፥21 እና ማብ ይመ):: *ፍሬ (የወይን) ... አይኖርም (በለስ)፤* የወይኑ ፍሬና የበለሱ ፍሬ እያንዳንዱ ሕዝብ የሚያመለክት ነው፤ ይኸውም በሚክ7፥1 ተጠቅሶአል፤ ም24 ይመ:: *ቅጠሎቻ ቸውም ይረግፋሉ፤* ከ17፥8፤ ከመዝ1፥3 ጋር ያገናዝቡ::

*8፥14-16፤* ነቢዩ የባቢሎናውያንን ወረራ ከወዲሁ በማየትና በኀሊና በመቃኘት ሕዝቡን ወክሎ የተናገረበት ክፍል ነው::

8፥14 *በአንድነት ተሰብሰቡ፤* 4፥5 ይመ:: ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ በቍ13 ላይ “... አልባ አደርጋቸዋለሁ” ከሚለው “ምርት” ከሚለው ጋር ከአንድ ሥርወ ቃል የወጡ በመሆናቸው፣ የቃላት ጨዋታ (ከሥነ ጽሑፍ ረገድ) ይታይ ባቸዋል:: *ወደ ተመሸጉት ከተሞች እንሽሽ፤* የ4፥5 ማብ ይመ:: *የተመረዘ ውሃ፤* ይህ ቃል በነቢዩ በኤርምያስ ዘንድ ብቻ ጥቅም ላይ የዋለ ነው (9፥15፤ 23፥15 ይመ፤ ከ25፥15 ጋር ያነጻጽሩ)::

*8፥15፤* በ14፥19 ከብዙ በጥቂቱ እንዳለ ተደግሞአል:: *ሰላምን፤* ከሁኔታው ጋር ሲስተያይ ባዶ ተስፋ ነበር (የ4፥10፤ 6፥14 ማብ ይመ):: *የፈውስ፤* የ6፥7 ማብ ይመ::

8፥16 *የጠላት ፈረሶች፤* የ4፥13 ማብ ይመ:: *ከዳን፤* ወደ ሰሜናዊ እስራኤል የሚገኝ ሩቅ ስፍራ ነው:: *የጠላት ፈረሶች፤* ይህ ሐረግ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “ኀያላኑ” የሚል ፍቺ ያስተከትላል፤ የዕብራይስጡ ቃል በ50፥11 “ድንጕላ ፈረስ”፣ በ47፥3፣ “የፈረስ ኰቴ” ተብሎ ተተርጕሞአል::

8፥17 *የአስማተኛ ብልኀት የማይገታቸው እፉኝቶች፤* ክፉዎችም ዘወትር እንደዚህ መሆናቸውን ለመግለጽ የገባ አገላ ለጽ ነው (መዝ58፥4-5 ይመ)::

*8፥18፤* እዚህ ላይ የሚናገረው ነቢዩ ነው:: *ልቤ በውስጤ ዝላለች፤* ሰ.ኤር1፥22፤ 5፥17 ይመ::

*8፥19፤* በዚህ ቍጥር የመጀመሪያ ክፍል ላይ የሚናገረው ነቢዩ ሲሆን፣ በቀሪው ክፍል ላይ የሚናገረው ግን እግዚአብሔር ነው:: *የሕዝቤን ... ከሩቅ ምድር፤* የይሁዳ ሕዝብ በምርኮ በባቢ ሎን ምድር እንደሚገኝ (የመዝ137፥1-4 ይመ)፣ ኤርምያስ አስቀድሞ በዐይነ ኀሊናው የቃኘው የወደፊት ሁኔታ ነው:: *እግዚ አብሔር በጽዮን የለምን?* ከሚክ3፥11 ጋር ያነጻጽሩ:: ሕዝቡ እግዚአብሔር ለምን ምድሩንና ቤተ መቅደሱን ለጥፋት እንደ ዳረገ አሁንም ግራ በመጋባት ላይ ነው (የ7፥4 ማብ ይመ):: *ንጉሥዋስ፤* እግዚአብሔርን ለማለት ነው (ኢሳ33፥22 ይመ):: *አስቈጡኝ፤* 7፥18፤ ዘዳ31፥29 ይመ:: *ከንቱ በሆኑ ባዕዳን፤* የ2፥5 ማብ ይመ::

*8፥20፤* ሕዝቡ ተስፋ አስቈራጭ በሆነው ምርኮ ውስጥ ሆነው የሚናገሩት ነው:: *እኛም አልዳንም፤* በምርኮ ጠላት እጅ ገብተናል ማለታቸው ነው::

*8፥21፤* ኤርምያስ በምርኮ ከተወሰዱት ወገኖች ጋር እንደ ተወሰደ አድርጎ ራሱን ይቈጥራል፤ ስሜታቸውንም ይናገራል:: *ያዘኝ፤* 6፥24 ይመ::

8፥22 *በገለዓድ የሚቀባ መድኀኒት፤* 46፥11፤ 51፥8 ይመ:: ገለዓድ ለቅመማ ቅመምና ለመድኀኒት የሚሆኑ ዕፀዋት የሚገኙበት ምድር ነበር (የዘፍ37፥25 ማብ ይመ):: *ቍስል ለምን ፈውስ አልተገኘም፤* ከ30፥17 ጋር ያገናዝቡ::

*9፥1-2፤* እዚህ ላይ ነቢዩ ስለ ወገኖቹ እያዘነ (ቍ1) ደግሞም ክፉ ተግባራቸው እያስቈጣው (ቍ2) ሲበሳጭ ይታያል::

*9፥1፤* ኤርምያስ ብዙውን ጊዜ የሚታወቀው፣ “አልቃሻው ነቢይ” በመባል ነው፤ ይህ መጠሪያ የሚገባው ነቢይ ነው (ቍ10፤ ሰቆቃወ ኤርምያስ ይመ፤ ከ2ሳሙ18፥33፤ ከማቴ23፥37፤ ከሮሜ 9፥2-4፤ 10፥1 ጋር ያነጻጽሩ)::

*9፥2፤* ነቢዩ በተቻለው መጠን ከክፉዎች ወገኖቹ እጅግ ለመራቅ ይፈልጋል (ከመዝ55፥6-8 ጋር ያነጻጽሩ):: *አመንዝሮች፤* የ2፥2 ማብ ይመ:: *የአታላዮች መንጋ፤* በጽሞና የሚካሄድን የአ ምልኮት ጉባኤ ለመግለጽ ይህ ቃል በዕብራይስጡ ትርጕም በብ ሉይ ኪዳን ላይ በሌላ ቦታ ውሎ ይገኛል (ለምሳ ዘዳ16፥8 ይመ)፤ ይሁንኑ ድርጊት ምእመናን አንዳንድ ጊዜ አጣመውት በመገኘታ ቸው ለፈጸሙት ጥፋት የመለኮት ፍርድ ደርሶባቸዋል (ኢሳ 1፥13፤ አሞ5፥21 ይመ):: *የአታላዮች፤* እግዚአብሔርን ለመበደል ያደረ ጉትን ሁኔታ ለመግለጽ ነው (የ3፥7 ማብ ይመ)::

[3]"ሐሰትን ለመናገር፣
ምላሳቸውን እንደ ቀስት ገተሩ፤
በእውነት ሳይሆን፣
በሐሰት በምድሪቱ ገነኑ፤
ከክፋት ወደ ክፋት ሄዱ፤
እኔንም አላወቁኝም፤"
ይላል እግዚአብሔር::
[4]"እያንዳንዱ ወንድም አታላይ[1]፣
ባልንጀራም ሁሉ ሐሜተኛ ስለ ሆነ፣
ወንድም ከወንድሙ፣ ይጠንቀቅ፣
ባልንጀራም በጓደኛው አይታመን::
[5]ባልንጀራ ባልንጀራውን ያታልላል፤
እውነትን የሚናገር የለም፤
ሐሰትን ይናገር ዘንድ ምላሳቸውን
አሠልጥነዋል፤
ኀጢአትንም በማድረግ ራሳቸውን
አድክመዋል::
[6]መኖሪያህ[2] በሽንገላ መካከል ነው፤
ከሽንገላቸውም የተነሣ ሊያውቁኝ
አልፈቀዱም፤"
ይላል እግዚአብሔር::
[7]ስለዚህ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፤ እንደ ብረት አነጥራቸዋለሁ፤
እፈትናቸዋለሁም፤
ስለ ሕዝቤ ኀጢአት፣
ከዚህ የተለየ ምን ማድረግ እችላለሁ?
[8]ምላሳቸው የሚገድል ቀስት ነው፤
በሽንገላ ይናገራል፤
ሁሉም ከባልንጀራው ጋር በፍቅር
ይናገራል፤
በልቡ ግን ያደባበታል::
[9]ታዲያ ስለ እነዚህ ነገሮች ልቀጣቸው
አይገባኝምን?"
ይላል እግዚአብሔር፤
"እንደዚህ ዐይነቱንስ ሕዝብ፣
አልበቀልምን?
[10]ስለ ተራሮች አለቅሳለሁ፤ ዋይ ዋይ
እላለሁ፤
በምድረ በዳ ስላሉትም መሰማሪያዎች
አዝናለሁ፤
ሰው የማያልፍባቸው ባድማ ሆነዋል፤
የከብቶች ጩኸት አይሰማም፤
የሰማይ ወፎች ሸሽተዋል፤
የዱር አራዊትም ጠፍተዋል::
[11]"ኢየሩሳሌምን የፍርስራሽ ክምር፣
የቀበሮም ጒሬ አደርጋታለሁ፤
የይሁዳንም ከተሞች፣
ሰው የማይኖርባቸው ባድማ
አደርጋቸዋለሁ::"

[12]ይህን መረዳት የሚችል ጥበበኛ ሰው ማን ነው? እግዚአብሔር ገልጾለት ይህንስ ማስረዳት የሚችል ማን ነው? ምድሪቱስ ሰው እንደማያልፍበት በረሓ ለምን ጠፋች? ለምን ወና ሆነች?

[13]እግዚአብሔርም እንዲህ አለ፤ "ይህ የሆነው የሰጠኋቸውን ሕጌን ትተው ስላል ታዘዙኝና ሥርዐቴን ስላልተከተሉ ነው:: [14]በዚህ ፈንታ፣ በልባቸው እልኸኝነት በመ ሄድ አባቶቻቸው ያስተማሯቸውን በአሊ ምን ተከተሉ::" [15]ስለዚህ የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣ እንዲህ ይላል፤ "እነሆ፤ ይህን ሕዝብ መራራ ምግብ አበላዋለሁ፤ የተመረዘንም ውሃ አጠጣዋ ለሁ:: [16]እነርሱንም ሆነ አባቶቻቸውን በማ ያውቋቸው ሕዝቦች መካከል እበትናቸዋ ለሁ፤ እስካጠፋቸውም ድረስ በሰይፍ አሳድ ዳቸዋለሁ::"

9፥3 ቍ 8፤ ዘፀ 20፥16፤መዝ 64፥3፤ ኢሳ1፥3፤44፥20፤ኤር 18፥18፤ሚክ6፥12
9፥4 ዘፍ 27፥35፤ ዘፀ20፥16፤ዘሌ19፥16፤ 2ሳሙ15፥12፤ሚክ 7፥5-6
9፥5 ዘሌ 6፥2፤ መዝ15፥2፤52፥3፤ኢሳ 59፥15
9፥6 ኤር 5፥27
9፥7 ኢዮ 28፥1፤ ኢሳ1፥25፤ኤር6፥27
9፥8 ቍ 3:4፤መዝ 35፥20፤ኢሳ3፥5፤ኤር 5፥26
9፥9 ዘዳ 32፥43፥ ኢሳ 10፥3
9፥10 ኤር 23፥10፤ ኢል1፥19፤ኤር4፥25፤ 12፥4፤ሆሴ4፥3፤ኢል 1፥18
9፥11 ዘሌ 26፥31፤ ኢዮ30፥29፤ኢሳ25፥ 2፤34፥13፤ኤር1፥15፤ 4፥13፤26፥9:18፤33፥ 10፤50፥3:13፤51፥62፤ ሰቆ1፥4
9፥12 መዝ 107፥43
9፥13 2ዜና 7፥19፤ መዝ89፥30-32
9፥14 ኤር 2፥8:23፤ 3፥17፤7፥24፤አሞ2፥4
9፥15 ኤር 8፥14፤ ሰቆ3፥15
9፥16 ዘሌ26፥33፤ ዘዳ4፥32፤ኤር8፥19፤ 14፥12፤24፥10፤44፥ 27፤ሕዝ5፥2:12

[1] 4 ወይም *አታላይ ያዕቆብ*
[2] 6 *ኤርምያስን ያመለክታል* (በዕብራይስጡ በነጠላ ቍጥር ተጽፏል)

*9፥3-9፤* በዚህ ክፍል የሚናገረው እግዚአብሔር ነው::

9፥3 *ምላሳቸውን እንደ ቀስት፤* ቍ5:8 ይመ፤ እንዲሁም መዝ64፥3-4፤ ያዕ3፥5-12 ይመ:: *እኔንም አላወቁኝም፤* ቍ6፤ መሳ2፥10፤ 1ሳሙ2፥12፤ ኢዮ18፥21፤ ሆሴ4፥1፤ ሮሜ1፥28 ይመ፤ ከሆሴ6፥3 ጋር ያገናዝቡ::

9፥4 *አታላይ፤* በዕብራይስጡ ይህ ቃል ከያዕቆብ ስም ጋር የተገናኘ ነው፤ ያዕቆብ ማለት "አታላይ" ማለት ነውና፤ ዘፍ 25፥26 እና ማብ፤ ሆሴ12፥2-3 ይመ::

9፥6 *ሊያውቁኝ አልፈቀዱም፤* ሁኔታቸው እየተባባሰ የሄደ ይመስላል (ቍ3 ላይ እኔን 'አላወቁኝም' ብቻ ነው የሚለው)

9፥7 *አነጥራቸዋለሁ፤ እፈትናቸዋለሁም፤* 6፥27-30 እና ማብ ይመ:: እግዚአብሔር ሕዝቡን "በመከራ እቶን" ይፈትና ቸዋል (ኢሳ48፥10 እና ማብ ይመ)::

9፥8 *ምላሳቸው ... በሽንገላ፤* ቍ3 እና ማብ ይመ:: *ይናገ ራል፤ በልቡ ግን፤* መዝ55፥21 ይመ:: *በፍቅር፤* ለዚህ የገባው የዕ ብራይስጥ ቃል በ6፥14 ላይ "ሰላም" ተብሎ ተተርጒሞአል (የዚ ያን ማብ ይመ)::

*9፥9፤* ከ5፥9:29 የተደገመ ነው::

*9፥10፤* እዚህ ላይ የሚናገረው ነቢዩ ነው:: የ4፥23-26 ማብ ይመ:: *አለቅሳለሁ፤ ዋይ ዋይ እላለሁ፤* ቍ18 ይመ፤ በተጨማሪም የቍ1 ማብ ይመ:: *በምድረ በዳ ስላሉትም መሰ ማሪያዎች፤* ጭራሹን መሰማሪያ ከማጣት የተሻለ ማለት ነው (1ሳሙ17፥28 ይመ፤ ከዘፀ3፥1 ጋር ያነጻጽሩ):: *ሰው የማያልፍ ባቸው፤* ቍ12፤ ሕዝ33፥28 ይመ:: *ባድማ፤* ይህን ቃል የሚተ ካው የዕብራይስጡ ቃል በቀሙ ሲተረጐም፣ "የተቃጠለ" ማለት ነው (በ2፥15 ላይ እንዳለው ማለት ነው)፤ እዚህ ላይ ግን በአን ገብጋቢው የፀሐይ ትኵሳት የነደደ ማለት ነው::

*9፥11፤* እዚህ ላይ የሚናገረው እግዚአብሔር ነው:: *የቀ በሮም ጒሬ፤* 10፥22፤49፥33፤51፥37፤መዝ44፥19፤ ኢሳ13፥21-22፤ ሰቆ5፥18፤ ሕዝ13፥4፤ሚል1፥3 ይመ፤ ከኢሳ35፥7 ጋር ያገናዝቡ:: *ሰው የማይኖርባቸው፤* 2፥15፤4፥7 እና ማብ ይመ::

*9፥12፤* ነቢዩ ጥያቄዎችን በተከታታይ ያቀርባል፤ *ጥበበኛ ሰው ማን ነው?* ሆሴ14፥9 ይመ::

*9፥13፤* እግዚአብሔር ለነቢዩ መልስ ከሰጠ በኋላ በቍ19 እስከ ሰፈረው ድረስ መናገሩ ይቀጥላል:: *የሰጠኋቸውን ሕጌን፤* በሙሴ ዘመን ማለት ነው (ዘዳ4፥8 ይመ)::

9፥14 *እልከኝነት፤* የ3፥17 ማብ ይመ:: *በኣሊም፤* 2፥23 ይመ፤ በተጨማሪም የመሳ2፥11 ማብ ይመ::

9፥15 *መራራ ምግብ አበላዋለሁ፤ የተመረዘንም ውሃ አጠ ጣዋለሁ፤* በ23፥15 ላይ ተደግሞአል፤ የ8፥14 ማብ ይመ:: ከመ ቶዎች ዓመታት በፊት ሙሴ እስራኤላውያን የዚህ ዐይነት ዕጣ ፈንታ እንዳይገጥማቸው አስጠንቅቆአቸው ነበር (ዘዳ 29፥18 ይመ)::

9፥16 *እበትናቸዋለሁ፤* 13፥24፤ 18፥17፤ 30፥11፤ 46፥28 ይመ:: ይህ ማስጠንቀቂያ ኪዳን ሲጣስ እንደሚደርስ እርግማን ሆኖ በዘዳ28፥64 ላይ ተሰጥቶአል:: *በሰይፍ አሳድዳቸዋለሁ፤* 42፥11 ይመ:: *እስካጠፋቸውም ድረስ፤* ሆኖም አንድም ሰው እንኳ እስከማይተርፍ ድረስ አይደለም (የ4፥27 ማብ ይመ፤ በተለይ 44፥27-28 ይመ)::

[17]የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

"እንግዲህ አስቡበት፤ አልቃሽ ሴቶች ጥሩ፤
*ሥ*ልጡን ሙሾ አውራጆች አስመጡ፤
[18]እነርሱ ፈጥነው ይምጡ፤
ዐይኖቻችን እንባ እስኪያጐርፉ፣
ሽፋሽፍቶቻችንም ውሃ እስኪያመነጩ፣
ስለ እኛ ሙሾ ያውርዱልን።
[19]እነሆ የዋይታ ድምፅ ከጽዮን ተሰምቶአል፤
እንዲህም ይላል፤
'ምንኛ ወደቅን!
ውርደታችንስ እንዴት ታላቅ ነው!
ቤቶቻችን ፈራርሰዋልና፤
አገራችንን ጥለን እንሂድ።' "
[20]እናንት ሴቶች ሆይ፤ *የእግዚአብሔርን*
*ቃ*ል ስሙ፤
ጆሮቻችሁን ከአንደበቱ ለሚወጡት
ቃላት ክፈቱ፤
ሴቶች ልጆቻችሁን ዋይታ፣
አንዳችሁም ሌላውን ሙሾ አስተምሩ።
[21]ሞት በመስኮቶቻችን ገብቶአል፤
ወደ ምሽጎቻችንም ዘልቆአል፤
ሕፃናትን ከየመንገዱ፣
ወጣቶችን ከየአደባባዩ ጠራርጎ ወስዶአል።
[22]እንዲህ በሉ፤ "*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
" 'የሰዎች ሬሳ፣
በሜዳ እንደተጣለ ጕድፍ፣
ማንም እንደማይሰበስበው፣
ከዐጫጅ ኋላ እንደተተወ ቃርሚያ
ይወድቃል።' "
[23]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"ጥበበኛ በጥበቡ አይታበይ፤
ኀያልም በኀይሉ አይመካ፤
ሀብታምም በሀብቱ አይኵራራ፤
[24]የሚመካ ግን፣
እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ
በማወቁና፣
በምድር ላይ ምሕረትን፣ ፍትሕንና
ጽድቅን የማደርግበት መሆኔን
በመረዳቱ፣
በዚህ ይመካ፤ እኔ በእነዚህ ነገሮች፣
እደሰታለሁና።"
ይላል *እግዚአብሔር*።

[25]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ሥጋቸውን ብቻ የተገረዙትን ሁሉ የምቀጣበት ጊዜ ይመጣል፤ [26]እነርሱም ግብፅ፣ ይሁዳ፣ ኤዶም፣ አሞን፣ ሞዓብና ጠጕራቸው ዙሪያውን የሚከረክም የበረሓ[a] ነዋሪዎች ሁሉ ናቸው፤ እነዚህ ሕዝቦች ሁሉ በእርግጥ የተገረዙ አይደሉምና፤ የእስራኤልም ቤት ሁሉ ልባቸው አልተገረዘም።

## ባዕድ አምልኮና እውነተኛው አምልኮ

10፥12-16 ተጓ ምብ-ኤር51፥15-19

**10** የእስራኤል ቤት ሆይ፤ *እግዚአብሔር* የሚላችሁን ስሙ። [2]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

"የአሕዛብን መንገድ አትከተሉ፤
እነርሱ በሰማይ ምልክቶች ይታወካሉ፣
እናንተ ግን በእነዚህ አትረበሹ።

[a]26 ወይም *በበረሓ በተራራቁ ስፍራዎች የሚኖሩ*

9፥17 መክ 12፥5
9፥18 መዝ 119፥136፤ሰቆ3፥48
9፥19 ኤር 4፥13
9፥20 ኢሳ32፥9-13፤ ኤር23፥16
9፥21 2ዜና36፥17፤ ኢሳ40፥30፤ኤር 16፥6፤ኢል 2፥9
9፥22 2ነገ 9፥37
9፥23 1ነገ 20፥11፤ ኢዮ4፥12፤መዝ62፥10፤ ምሳ11፥28፤ መክ9፥11፤ኤር48፥7፤ 49፥4፤ ሕዝ 28፥4-5
9፥24 መዝ 34፥2፤ መዝ36፥6፡10፡51፥1፤ 1ቆሮ1፥31፤ 2ቆሮ 10፥17፤ገላ6፥14
9፥25 ዘሌ 26፥41፤ ሮሜ2፥25
9፥26 1ሳሙ 14፥6፤ ኤር25፥23፤49፥32፤ ሕዝ 31፥18፤ ሐሥ 7፥51
10፥2 ዘፍ 1፥14፤ ዘዐ23፥24፤ዘሌ20፥23

9፥17 *አልቃሽ ሴቶች፤* ሰው ሲሞት ወይም በሌላ አሳዛኝ ሁኔታ በገንዘብ ተቀጥረው ሌላውን የሚያስለቅሱ ነበሩ (2ዜና 35፥25፤ መክ12፥5 አሞ5፥16 ይመ)።

*9፥18፤* አልቃሾች በገንዘብ የሚቀጠሩት ዘመድ የሞተ ባቸውን ለማስለቀስና ለማስተከዝ ነበር። *ሙሾ ያውርዱልን፤* ቍ 10 ይመ። *ዐይኖቻችን እንባ እስኪያጐርፉ፤* ቍ 1 ይመ።

9፥19 *ምንኛ ወደቅን!* 4፥13፡20፤ 48፥1 ይመ።

*9፥20-21፤* በዚህ ክፍል የሚናገረው ነቢዩ ነው።

*9፥20፤* ብዙ አልቃሽ ስለሚያስፈልግ በሐዘን ላይ ያሉት ሴቶች እንዴት እንደሚለቀስ ሴቶች ልጆቻቸውን ማስተማር አለ ባቸው።

9፥21 *ሞት፤* እዚህ ላይ ሞት በሰው ተመስሎአል (በዕ ንጋ2፥5 ላይ እንዳለው ማለት ነው)። በከነዓን አገር ስሙ "ሞት" የሚባል ጣዖት ነበር፤ የመካንነትና የሙታን ዓለም አምላክ ተብሎ ይታመን ነበር። ይህ ስም በዕብራይስጥ "መሞትን" ያመለክታል። *በመስኮቶቻችን ገብቶአል፤* በኢል 2፥9 ላይ ይህ አባባል የጠላት ወታደሮችን ድርጊት ለመግለጽ ውሎአል። *ሕፃናትን ... ወጣቶችን፤* 6፥11 ይመ።

9፥22 *የሰዎች ሬሳ፤* 7፥33 እና ማብ ይመ። *እንደ ... ጕድፍ፤* የ8፥2 ማብ ይመ። *ከዐጫጅ፤* ሞት፣ "ጨካኝ ዐጫጅ ነው" የሚለው ሐሳብ በአብዛኛው ከዚህ ጥቅስ የመጣ ነው።

9፥23 *ጥበበኛ ... ሀብታምም በሀብቱ አይኵራራ፤* ይህ አባባል ከኤርምያስ ዘመን ከመቶ ዓመት ገደማ በኋላ በተጻፉ የዕ ብራይስጥ ጽሑፎች ከብዙ በጥቂቱ እንዳለ ተደግሞ ይገኛል።

*9፥24፤* 1ቆሮ1፥31 "የሚመካ በእግዚአብሔር ይመካ" በማ ለት በአጭሩ አስቀምጦታል። *በእነዚህ፤* የኋላ ኋላ ዋጋ የሚኖረው እግዚአብሔርን ማወቃችንና እርሱን መውደዳችን ነው። *በማወቁና ... መረዳቱ፤* 3፥15 ይመ። እንዲሁም የ4፥22 ማብ ይመ። *እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ፤* የድነት ወይም የመዋጀት ትምህርት የሚገኝበት ዋነኛ ክፍል የሆነው ዘፀ6፥2-8 የሚጀምረውም የሚደመድመውም በዚሁ እግዚአብሔር ራሱን በገለጸበት አባባል ነው። *ምሕረትን፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በ2፥2 ላይ፣ "ታማኝ" ተብሎ ተተርጕሞአል (የ2፥2 ማብ ይመ)። *በእነዚህ ... እደሰታለሁና፤* መዝ11፥7፤ 33፥5፤ 99፥4፤ 103፥6፤ ሚክ6፥8፤ 7፥18 ይመ።

*9፥25-26፤* ሮሜ2፥25-29 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ17፥10 ማብ ይመ።

9፥26 *ጠጕራቸው ዙሪያውን የሚከረክም የበረሓ ነዋሪዎች፤* የዓረብ ወገኖች ሲሆኑ (25፥23፤ 49፥32 ይመ)፣ ኋላ በናቡከደነፆር የተመሩት ባቢሎናውያን ወግተዋቸዋል (49፥28-33 ይመ)፤ ከዘሌ19፥27 ጋር ያነጻጽሩ። *ልባቸው አልተገረዘም፤* 4፥4 እና ማብ ይመ።

*10፥1-25፤* ኤርምያስ በቤተ መቅደስ አካባቢ ያስተላለ ፈውን ተከታታይ መልእክት በግጥም መልክ እዚህ ላይ ይደመድ ማል፤ ይህም ክፍል በጣዖታትና በእግዚአብሔር መካከል ባለው እጅግ ታላቅ ልዩነት ላይ ያተኰረ ነው (ቍ 2-16)። ጣዖታትና እነርሱን የሚያመልኩ ሰዎች ተወግዘዋል (ቍ 2-5፡ 8-9፡11፡14-15)፤ በአንጻሩ አንዱ አምላክ እግዚአብሔር በአማራጭ የጽሑፍ ክፍሎች ተመስግኖአል፤ ተወድሶአልም (ቍ 6-7፡10፡12-13፡16)። ኢሳ40፥18-20፡ 41፥7፤ 44፥9-20፤ 46፥5-7 ይመ።

10፥1 *ስሙ፤* የ2፥4 ማብ ይመ።

10፥2 *የአሕዛብን ... አትረበሹ፤* 1፥17 ይመ። *መንገድ፤* ይህ ቃል የሚያመለክተው የሕዝቡን የሃይማኖት ሥርዐት አፈጻጸም ነው። የመጀመሪያዎቹ ክርስቲያኖች ልዩ እምነታቸውን፣ "መንገዱ" ብለው ይጠሩት ነበር (ሐሥ9፥2፤ 19፥9፡23፤ 22፥4፤ 24፥14፡22 ይመ)። *በሰማይ ምልክቶች፤* በሰማይ ያሉ፣ በዐይን የማ ይታዩ ግዑዛን ፍጥረታትን እግዚአብሔር አበጅቶ ያስቀመጣቸው ለሌላ ዐላማ እንጂ፣ እንዲመለኩ አልነበረም (ዘፍ1፥14-18 እና ማብ ይመ)። *እነርሱ ... ይታወካሉ፤* በራሳቸው በሰማይ ከዋክብት ብቻ ሳይሆን፣ አንዳንድ ጊዜ በሚከሠቱት ባሕ ርዮቻቸው ጭምር ማለት ነው (ይኸውም እንደ ጅራታም ኮከብ፣ እንደ ተወርዋሪ ኮከብ እንደ ፀሓይና ጨረቃ ግርዶሽ

[3]የአሕዛብ ልማድ ከንቱ ነውና፤
ዛፍ ከጫካ ይቈርጣሉ፤
አናጺም በመሣሪያው ቅርጽ ያበጅለታል፤
[4]በብርና በወርቅ ይለብጡታል፤
እንዳይወድቅም፣
በመዶሻ መትተው በምስማር
ያጣብቁታል።
[5]ጣዖቶቻቸው በዱባ ዕርሻ መካከል እንደ
ቆመ ማስፈራሪያ ናቸው፤
የመናገር ችሎታ የላቸውም፤
መራመድም ስለማይችሉ፣
ተሸካሚ ያስፈልጋቸዋል፤
ጕዳት ማድረስም ሆነ፣
መልካምን ነገር ማድረግ ስለማይችሉ፣
አትፍሯቸው።"
[6]እግዚአብሔር ሆይ፤ እንዳንተ ያለ ማንም
የለም፤
አንተ ታላቅ ነህ፤
የስምህም ሥልጣን ታላቅ ነው።
[7]የሕዝቦች ሁሉ ንጉሥ ሆይ፤
አንተን የማይፈራ ማነው?
ክብር ይገባሃልና።
ከምድር ጠቢባን ሁሉ፣
ከመንግሥቶቻቸውም ሁሉ መካከል፣
እንዳንተ ያለ የለም።
[8]ከከንቱ የዕንጨት ጣዖት ትምህርት
የሚቀስሙ ሁሉ፣
ጅሎችና ሞኞች ናቸው።
[9]የተጠፈጠፈ ብር ከተርሴስ፣
ወርቅም ከአፌዝ ይመጣል።
ባለሙያውና አንጥረኛው የሠሯቸው፣
ብልኀተኞችም ያበጇቸው ሁሉ፣
ሰማያዊና ሐምራዊ ልብስ ተጐናጽፈዋል።
[10]እግዚአብሔር ግን እውነተኛ አምላክ ነው፤
እርሱ ሕያው አምላክ፣ ዘላለማዊም ንጉሥ
ነው፤
በሚቈጣበት ጊዜ ምድር ትንቀጠቀጣለች፤
መንግሥታትም ቍጣውን ሊቋቋሙ
አይችሉም።

[11]"እናንተም፣ 'እነዚህ ሰማያትንና ምድ ርን ያልፈጠሩ አማልክት ከምድር ላይ፣ ከሰ ማያትም በታች ይጠፋሉ' ትሏቸዋላችሁ።"[h]

[12]እግዚአብሔር ግን ምድርን በኀይሉ ፈጠረ፤
ዓለምን በጥበቡ መሠረተ፤
ሰማያትንም በማስተዋሉ ዘረጋ።
[13]ድምፁን ሲያንጐደጕድ፣ በሰማያት ያሉ
ውሆች ይናወጣሉ፤
ጉሙን ከምድር ዳር ወደ ላይ እንዲወጣ
ያደርገዋል፤
መብረቅን ከዝናብ ጋር ይልካል፤
ነፋስንም ከግምጃ ቤቱ ያወጣል።
[14]እያንዳንዳቸው ጅሎችና ዕውቀት የለሾች
ናቸው።
ወርቅ አንጥረኛውም ሁሉ በሠራው
ጣዖት አፍሮአል፤
የቀረጻቸው ምስሎቹ የሐሰት ናቸው፤
እስትንፋስም የላቸውም።
[15]እነርሱ ከንቱ የፌዝ ዕቃዎች ናቸው፤

[h]11 ይህ ጥቅስ የተጻፈው በአራማይክ ቋንቋ ነው

10፥3 ዘዳ9፥21፤1ነገ 8፥36፤ኢሳ 40፥19፤ ኤር44፥8፤ሕዝ7፥20
10፥4 1ሳሙ 5፥3፤ መዝ135፤ 15፤ኢሳ 41፥7፤ሆሴ13፥2፤ዕን 2፥19
10፥5 1ነገ 18፥26፤ ኢሳ45፥20፤ 41፥23፡ 24፤44፥9-20፤ 46፥7 1ሐሥ19፥26፤ 1ቆሮ 12፥2
10፥6 ዘፀ 8፥10፤ 2ሳሙ7፥22፤መዝ 48፥1
10፥7 መዝ 22፥28፤ ኢሳ12፥4፤ኤር5፥22፤ ራእ15፥4
10፥8 ዘዳ 32፥21፤ ኢሳ44፥18፤40፥19፤ ኤር 4፥22
10፥9 ዘፍ 10፥4፤ መዝ115፥4፤ ኢሳ 40፥19
10፥10 ዘፍ21፥33፤ ኢሱ3፥10፤ መሳ5፥4፤ ኢዮ9፥6፤መዝ18፥7፤ 29፥8፤76፥7፤ኤር 21፥12፤ዳን 6፥26፤ ናሆ1፥6፤ማቴ16፥16
10፥11 ኢሳ 2፥18
10፥12 ቍ16፤ ዘፍ 1፥1፡8፡31፤1ሳሙ2፥8
10፥13 ዘዳ 28፥12፤ ኢዮ36፥29፡30፤መዝ 104፥13፤135፥7
10፥14 መዝ97፥7፤ ኢሳ1፥29፤44፥20
10፥15 ኢሳ41፥24፤ ኤር14፥22

ያሉ ማለት ነው)።

10፥3 *ከንቱ፤* ኤርምያስ ጣዖታትን ለመግለጽ ብዙ ጊዜ የሚጠቀምበት ቃል ነው (ቍ8፡15 ይመ፤ እንዲሁም የ2፥5 ማብ ይመ)። *ዛፍ ... ይቈርጣሉ፤* ኢሳ44፥14-15 ይመ። *አናጺም፤* ቃሉ ጣዖታትን ከእንጨት የሚያበጁትን ሰዎች የሚያመለክት ነው፤ እነዚህ ሰዎች ሁልጊዜም ባይሆን (ኢሳ40፥19 ይመ)፣ እንጨት ጠርበው ጣዖታትን የሚያበጁ ናቸው (ኢሳ41፥7 ይመ)። *መሣሪያ፤* ከኢሳ44፥13 ጋር ያነጻጽሩ።

10፥4 *በብርና በወርቅ፤* ከእንጨት የተሠሩ የጣዖታት ምስሎች በውድ ብረታ ብረት ተለብጠው ውበታቸው እንዲ ጨምር ይደረግ ነበር (ኢሳ30፥22፤ 40፥19 ይመ)። *እንዳይ ወድቅም ... ያጣብቁታል፤* ኢሳ40፥20፤ 41፥7 ይመ፤ ከ46፥7 ጋር ያነጻጽሩ፤ ከ1ሳሙ5፥2-4 ጋር ያገናዝቡ።

*10፥5፤* ጣዖታት አንዳች ነገር ማድረግ ስለ አለመቻላቸው በመዝ115፥4-7፤ 135፥15-18 ላይ ጊዜ በማይሽረው አገላለጽ ተብ ራርቶአል። *ማስፈራሪያ፤* ፀረ ሰብል የሆኑ አራዊት ማሳ ውስጥ ገብተው እህል እንዳይበሉ ወይም እንዳያበላሹ በሰው ቅር ጽ የሚተከል ማስደንገጫ ምስል ነው። *በዱባ እርሻ፤* ኢሳ1፥8 እና ማብ ይመ። *ተሸካሚ ያስፈልጋቸዋል፤* ብዙውን ጊዜ በክብት ይጫናሉ፤ ኢሳ46፥1 ይመ። *ጕዳት ... መልካምን፤* ጣዖታት አንዳች ነገር ሊሠሩ አይችሉም (ኢሳ41፥23 ይመ)።

10፥6 *ማንም፤* ከአማልክት መካከል እንደርሱ ያለ የለም ማለት ነው (መዝ86፥8 ይመ)። *የስምህም ሥልጣን ታላቅ ነው፤* 16፥21 ይመ።

10፥7 *የሕዝቦች ሁሉ ንጉሥ፤* መዝ47፥8-9፤ 96፥10 ይመ። አስፈሪነታቸው በቀበሌያቸው እንደሚወሰነው፣ እንደ ነገዶች አማልክት ሳይሆን፣ እግዚአብሔር የሁሉ ንጉሥ ነው። *ከምድር ጠቢባን ሁሉ ... እንዳንተ ያለ የለም፤* ኢሳ19፥12፤ 29፥14፤ 1ቆሮ1፥20 ይመ።

10፥8 *ከንቱ፤* የቍ3 ማብ ይመ። *ከ ... ጣዖታት ትምህርት የሚቀስሙ፤* ከእግዚአብሔር በመማር ፈንታ (ዘዳ 11፥2፤ ኢዮ5፥17፤ ምሳ3፥11 ይመ)። *ጅሎችና ሞኞች፤* ቍ14፥ 21፤ 5፥21 ይመ።

10፥9 ... *ብር ከተርሴስ፤* ሕዝ27፥12 ይመ፤ የኢሳ23፥6፤ የዮና1፥3 ማብ ይመ። *ከአፌዝ፤* ይህ ስም ተጠቅሶ የሚገኘው እዚህ ብቻ ነው፤ የት እንደሆነ ቦታው አይታወቅም። *ባለሙያውና አንጥረኛው፤* ኢሳ40፥19፤ 41፥7 ይመ። *ሰማያዊና ሐምራዊ ልብስ ተጐናጽፈዋል፤* ግርማ ያለው ንጉሥ እንዲመስል ማለት ነው። *ሁሉ፤* ጣዖታቱን ለማለት ነው።

*10፥10፤* ጣዖታት ሊሆኑ የማይችሉትን ሁሉ ጌታ እግዚ አብሔር ግን መሆን ይቻለዋል። *እውነተኛ፤* 1ተሰ1፥9 ይመ። *ሕያው፤* ዘዳ5፥26 ይመ። *ዘላለማዊም፤* ዘፀ15፥18፤ መዝ10፥16፤ 29፥10 ይመ። *በሚቈጣበት ጊዜ ... አይችሉም፤* መዝ97፥5፤ ናሆ1፥5 ይመ።

*10፥11፤* ይህ ቍጥር በአራማይክ ቋንቋ የተጻፈ ነበር። በብሉይ ኪዳን ውስጥ በአራማይክ ተጽፈው የሚገኙ ሌሎች ክፍሎች፡- ዕዝ4፥8-6፥18፤ 7፥12-16፤ ዳን2፥4-7፥28 ናቸው። ይኸ ኛው ቍጥር በስድ ንባብ የተጻፈ ነው። *ትሏቸዋላችሁ፤* በዚህ ግሥ ውስጥ ያለው የብዙ ቍጥር ሦስተኛ መደብ (ለእነርሱ) ጣዖት አምላኪ የሆኑ አሕዛብን የሚያመለክት ነው፤ ከዕብራይስጥ ይልቅ በጊዜው የብዙ አገሮች የጋራ ቋንቋ የነበረውን አራማይክ የሚያውቁ ሳይሆን አልቀሩም።

*10፥12-16፤* በ51፥15-19 ላይ እንዳለ ተደግሞአል።

10፥12 *እግዚአብሔር ግን፤* በቍ11 ላይ ካሉት ከሐሰተኛ አማልክት አንጻር ማለት ነው። *ሰማያትንም ... ዘረጋ፤* እንደ ድንኳን ወይም እንደ መጋረጃ (መዝ104፥2፤ ኢሳ40፥22 እና ማብ ይመ)።

10፥13 *ጉሙን ... ከግምጃ ቤቱ ያወጣል፤* በመዝ135፥7 ላይ ተደግሞአል፤ በዚያ እውነተኛው አምላክ ከሐሰት አማልክት ጋር በንጽጽር መልክ ቀርቦአል (መዝ135፥5፡15-17 ይመ፤ ከኢዮ 38፥22 ጋር ያነጻጽሩ)።

10፥14 *ጅሎች፤* ቍ8፡21 ይመ፤ እንዲሁም የ4፥22 ማብ ይመ። *ምስሎቹ፤* ከብረታ ብረት የተበጁ ቅርጻ ቅርጾች ናቸው፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በኢሳ48፥15 ላይ "የብረታ ብረት ቅርጾች" ተብሎአል። *እስትንፋስም የላቸውም፤* መዝ 135፥17 ይመ።

10፥15 *ከንቱ፤* የቍ3 ማብ ይመ።

ፍርድ ሲመጣባቸው ይጠፋሉ።
[16]የያዕቆብ ዕድል ፈንታ የሆነው ግን
እንደነዚህ አይደለም፤
እርሱ የሁሉ ነገር ፈጣሪ ነውና፤
እስራኤልም የርስቱ ነገድ ነው።
ስሙ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ነው።

## ሊመጣ ያለው ግዞት

[17]አንቺ የተከበብሽ፤
ከያለበት ንብረትሽን ሰብስቢ፤
[18]እግዚአብሔር እንዲህ ይላልና፤
"በዚህች ምድር የሚኖሩትን፣
አሁን ወደ ውጪ እወነጭፋቸዋለሁ፤
ጉዳቱ እንዲሰማቸው፣
መከራ አመጣባቸዋለሁ።"
[19]ስለ ስብራቴ ወዮልኝ፤
ቍስሌም የማይድን ነው፤
ግን ለራሴ እንዲህ አልሁት፤
"ይህ የኔው ሕመም ነው
ልሸከመውም ይገባኛል።"
[20]ድንኳኔ ፈርሶአል፤
ገመዶቹም ሁሉ ተበጣጥሰዋል፤
ልጆቼ ጥለውኝ ሄደዋል፤ ከእንግዲህም
አይመለሱም፤
ድንኳኔን ለመትከል፣
መጋረጃዬንም ለመዘርጋት ማንም የቀረ
የለም።
[21]እረኞቹ አእምሮ የላቸውም፤
እግዚአብሔርን አይጠይቁም፤
ስለዚህ አልተከናወነላቸውም፤
መንጎቻቸውም ሁሉ ተበታትነዋል።
[22]መርዶ ስሙ! እነሆ፤ ከሰሜን ምድር፣
ታላቅ ሸብር እየመጣ ነው፤
የይሁዳን ከተሞች ባድማ፣
የቀበሮዎችም መናኸሪያ ያደርጋል።

## የኤርምያስ ጸሎት

[23]እግዚአብሔር ሆይ፤ የሰው ሕይወት
በራሱ እጅ እንዳልሆነች፣
አካሄዱንም በራሱ አቃንቶ ሊመራ
እንደማይችል ዐውቃለሁ።
[24]እግዚአብሔር ሆይ፤ ቅጣኝ፤ ብቻ በመጠኑ
ይሁንልኝ፤
ፈጽሞ እንዳልጠፋ፣
በቍጣህ አትምጣብኝ።
[25]ያዕቆብን አሟጠው ስለበሉት፣
ፈጽመው ስለዋጡት፣
መኖሪያውንም ወና ስላደረጉ፣
በማያውቁህ ሕዝቦች፣
ስምህንም በማይጠሩ ወገኖች ላይ፣
ቍጣህን አፍስስ።

## ያልተከበረው ኪዳን

11 ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ ኤርምያስ የመጣው ቃል ይህ ነው፤ [2]"የዚህን ኪዳን ቃል ስማ፤ ለይሁዳ ሕዝብና በኢየሩሳሌም ለሚኖሩ ሰዎች ንገራቸው፤ [3]የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል በላቸው፤ 'ለዚህ ኪዳን ቃል የማይታዘዝ ሰው የተረገመ ይሁን፤ [4]ይህም ትእዛዝ የቀድሞ አባቶቻችሁን ከግብፅ ምድር፣ ከብረት ማቅለጫው ምድጃ ባወጣኋቸው ጊዜ ድምፄን ቢሰሙ፣ ትእዛዜንም ሁሉ ቢጠብቁ፣ እነርሱ ሕዝቤ፣ እኔም አምላካቸው እንድሆን የሰጠኋቸው ቃል ነው፤ [5]ዛሬም እንደ ሆነው ሁሉ ወተትና ማር የምታፈሰውን ምድር ለአባቶቻችሁ ለመስጠት የገባሁትን መሐላ

10፥16 ቍ12፤ዘፀ 34፥9፤ዘዳ32፥9፤መዝ 74፥2፤119፥57፤ኤር 31፥35፤32፥17፡18፤ 33፥2
10፥17 ሕዝ12፥3-12
10፥18 ዘዳ 28፥52፤ 1ሳሙ25፥29፤ኢሳ 22፥17፤
10፥19 ኢዮ34፥6፤ ኤር14፥17፤15፥18፤ 30፥12፡15፤ሰቆ2፥13፤ ሚክ1፥9፤7፥9፤ናሆ 3፥19
10፥20 ኤር4፥20፤ 31፥15፤ሰቆ1፥5
10፥21 ቍ8፤ኢሳ 56፥10፤ኤር22፥22፡ 30፤23፥1፡2፤25፥34፤ 50፥6፤ሕዝ34፥6
10፥22 ኢሳ34፥13፤ ኤር6፥22፤27፥6፤49፥ 28፡30፤ሕዝ12፥19
10፥23 ኢዮ33፥29፤ ምሳ3፥5-6፤20፥24
10፥24 መዝ6፥1፤ 38፥1፤ኤር7፥20፤18፥ 23፤46፥28፤30፥11
10፥25 መዝ14፥4፤ 69፥24፤79፥6-7፤ኤር 2፥3፤ሶፎ2፥2፤3፥8
11፥2 ዘዳ 5፥2
11፥3 ዘዳ11፥26-28 ፤27፥26፤28፥15-68፤ ገላ3፥10
11፥4 ቍ7፤ዘፀ24፥8 ፤1ነገ8፥51፤ኤር7፥23 ፤31፥33፤ሕዝ11፥20
11፥5 ዘፀ3፥8፤6፥8 ፤13፥5፤ዘዳ7፥12፤27 ፥26፤መዝ105፥8-11

10፥16 *የያዕቆብ ዕድል ፈንታ፤* የእግዚአብሔር መጠሪያ ሲሆን፣ ሌላ ቦታ ጥቅም ላይ ውሎ የሚገኘው በ51፥19 ላይ ብቻ ነው (መዝ73፥26፤ 119፥57፤ 142፥5፤ ሰቆ3፥24 ይመ)። *የርስቱ ነገድ፤* ኢሳ63፥17 ይመ። *ስሙ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ነው፤* ኢሳ54፥5፤ አሞ4፥13 ይመ።

*10፥17-22፤* መጥፋትና መማረክ እጅግ ተቃርቦአል፤ አይቀሬም ነው።

10፥18 *እወነጭፋቸዋለሁ፤* ልክ ድንጋይ ከውንጭፍ ፈትለክ ብሎ እንደሚወጣ ማለት ነው።

*10፥19-20፤* ነቢዩ ስለ ወገኖቹና ስለ ራሱም ዕጣ ፈንታ በሐዘን ተውጦአል(4፥19-21 ይመ)።

10፥20 *ልጆቼ፤* የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን ሕዝብ የሚመለከት ነው። ኤርምያስ ከቶ አላገባም፤ ልጆችም አልነበሩትም (16፥2 ይመ)። *መጋረጃዬንም፤* የ4፥20 ማብ ይመ።

10፥21 *እረኞቹ ... መንጎቻቸውም፤* ገዦቹና ሕዝቡን ለማለት ነው (የ2፥8 ማብ ይመ)። *አእምሮ የላቸውም፤* ቍ8፡14 ይመ፤ እንዲሁም የ4፥22 ማብ ይመ። *እግዚአብሔርን አይጠይቁም፤* በዚህ ፈንታ የሰማይን ሰራዊት (ከዋክብትንና ጨረቃን) ይጠይቃሉ (8፥2 ይመ)። *ተበታትነዋል፤* የ9፥16 ማብ ይመ።

10፥22 *ከሰሜን ምድር፤* የባቢሎን ምድር ነው (4፥6፤ 6፥22 ይመ)፤ እንዲሁም የኢሳ41፥25 ማብ ይመ)። *ታላቅ ሸብር፤* የወራሪዎቹ ድምፅ ነው (6፥23፤ 8፥16 ይመ)። *የቀበሮዎችም መናኸሪያ፤* 9፥11 እና ማብ ይመ።

*10፥23-25፤* ኤርምያስ ሕዝቡን በመወከል፣ የእግዚአብሔር ቅን ፍርድ እንዲመጣ ይጸልያል።

*10፥23፤* የሰውን/አካሄድ ሊመራና ሊቈጣጠር የሚችል እግዚአብሔር ብቻ ነው (መዝ37፥23፤ ምሳ16፥9 ይመ)።

*10፥25፤* ይህ አባባል በመዝ79፥6-7 ላይ እንዳለ ተደግሞአል፤ ዐውዱ (መዝ79፥1-5) እንደሚያሳየው፣ መዝሙሩ ጭፍን በቀል ሳይሆን፣ የእግዚአብሔር ቅን ፍርድ እንዲገኝ የቀረበ ልመና ነው፤ አይሁድ ይህን ጥቅስ በየዓመቱ በፋሲካ ሥርዐት ላይ ይደግሙታል።

*11፥1-13፥27፤* ይሁዳ የገባችውን ኪዳን በመጣስ ስላመፀች፣ ሕዝቡ ወደ ባቢሎን ምርኮ ይወሰዳል። ይህ ክፍል በኢዮስያስ ዘመን ስለ ነበረው ሁኔታ የሚናገር ሳይሆን አይቀርም (ይሁን እንጂ የ13፥18 ማብ ይመ)።

*11፥1-17፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ ከአምላካቸው ጋር የገቡትን ኪዳን እንዳልጠበቁ የሚያሳይ ክፍል ነው።

11፥2 *የዚህን ኪዳን፤* ቍ3፡6፡8፡10፤ ዘዳ29፥9 ይመ። እዚህ ላይ የሚያመለክተው እግዚአብሔር ከእስራኤል ሕዝብ ጋር በሲና ተራራ የመሠረተውንና ያጸናውን ኪዳን ነው (ቍ4፤ ዘፀ19-24 ይመ)። *ቃል፤* የኪዳኑን ውል ለማለት ነው (ቍ3-4፡6፤ 34፥18 ይመ፤ የዘፀ20፥1 ማብ በተጨማሪ ይመ)። *ስማ፤* የ2፥4 ማብ ይመ። *ንገራቸው፤* የኪዳኑን ቃል በየጊዜውና በየወቅቱ ለሕዝቡ ማንበብ የተለመደና አስፈላጊም ነበር (ዘዳ31፥10-13፤ኢሳ8፥34-35 ይመ)።

11፥3 ... *የማይታዘዝ ሰው የተረገመ ይሁን፤* በዘዳ27፥15-26 ይህ ሐረግ በእያንዳንዱ ቍጥር መጀመሪያ ላይ ይገኛል ("አሜን" የሚለው ቃል በመጨረሻው ላይ ይገኛል፤ የቍ5 ማብ ይመ)። ለኪዳኑ መታዘዝ በረከትን ያስከትላል (ዘዳ28፥1-14 ይመ)፤ እርግማን የሚመጣው ለኪዳኑ ባለመታዘዝ ነበር (ዘዳ 28፥15-68 ይመ፤ በተጨማሪም ዘዳ11፥26-28፤29፥20-21 ይመ)።

11፥4 *ከግብፅ ምድር፣ ከብረት ማቅለጫው ምድጃ ...፤* የዘዳ4፥20 ማብ ይመ። *ትእዛዜንም ... ቢጠብቁ፤* ቍ7፤ 7፥23፤ ዘፀ19፥5 ይመ። *እነርሱ ሕዝቤ፣ እኔም አምላካቸው፤* የ7፥23 ማብ ይመ።

11፥5 *ወተትና ማር የምታፈሰውን ምድር፤* 32፥22 ይመ፤

እፈጽማለሁ::’ ”

እኔም፣ “*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አሜን” ብዬ መለስሁ::

[6]*እግዚአብሔር*ም እንዲህ አለኝ፤ “ይህን ቃል ሁሉ በይሁዳ ከተሞችና በኢየሩሳሌም አደባባዮች ተናገር፤ እንዲህም በል፤ ‘የዚህን ኪዳን ቃል ስሙ፤ አድርጉትም፤ [7]የቀድሞ አባቶቻችሁን ከግብፅ ምድር ካወጣሁበት ጊዜ ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ፣ “ታዘዙኝ” በማለት ደጋግሜ አስጠንቀቅኋቸው:: [8]እነርሱ ግን የክፉ ልባቸውን እልከኝነት ተከተሉ እንጂ አልታዘዙኝም፤ ጆሮአቸውንም ወደ እኔ አላዘነበሉም፤ ስለዚህ እንዲከተሉት አዝዤአቸው ያላደረጉትን የዚህን ኪዳን ርግማን ሁሉ አመጣሁባቸው::’ ”

[9]*እግዚአብሔር*ም እንዲህ አለኝ፤ “በይሁዳ ሕዝብና በኢየሩሳሌም ነዋሪዎች ዘንድ አድማ ተገኝቶአል:: [10]ቃሌን መስማት ወዳልፈለጉት ወደ ቀድሞ አባቶቻቸው ኀጢአት ተመለሱ፤ ሊያገለግሏቸውም ሌሎችን አማልክት ተከተሉ:: የእስራኤልና የይሁዳ ቤት ከቀድሞ አባቶቻቸው ጋር የገባሁትን ኪዳን አፈረሱ:: [11]ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ‘ሊያመልጡት የማይችሉትን ጥፋት አመጣባቸዋለሁ፤ ወደ እኔ ቢጮኹም አልሰማቸውም:: [12]የይሁዳ ከተሞችና የኢየሩሳሌም ሕዝቦች ወደሚያጥኑላቸው አማልክት ሄደው ይጮኻሉ፤ እነርሱ ግን በመከራቸው ጊዜ ከቶ ሊረዷቸው አይችሉም:: [13]ይሁዳ ሆይ፤ የአማልክትህ ቍጥር የከተሞችህን ብዛት ያህል ነው፤ አሳፋሪ ለሆነው ጣዖት፣ ለበኣል ማጠኛ የሠራችኋቸው መሠዊያዎቻችሁ ብዛት የኢየሩሳሌምን መንገዶች ያህል ነው::’ ”

11፥6 ዘዐ 15፥26፤ ዘዳ15፥5፤ኤር 4፥5፤ ያዕ1፥22
11፥7 2ዜና 36፥15
11፥8 ዘሌ26፥14-43 ፤ዘዳ28፥15-68፤ኢሱ 23፥15፤ 2ዜና7፥19፤ መዝ78፥10፤መክ9፥3፤ ኤር3፥17፤7፥26፤26፥4፤32፥23፤44፥10
11፥9 ሕዝ 22፥25
11፥10 ዘዳ 9፥7፤ መሳ2፥12-13፤10፥13 ፤2ዜና30፥7፤ኢሳ24፥5 ፤ኤር16፥11፤34፥18፤ ሕዝ20፥8፤ሆሴ 6፥7፤ 8፥1፤ ዘካ 7፥11
11፥11 ቍ14፤ 2ነገ 22፥16፤ኢዮ 11፥20፤ 27፥9፤መዝ66፥18፤ ምሳ1፥28፤ኢሳ1፥15 ፤59፥2፤ኤር 14፥12፤ 4፥6፤ሰቆ2፥22፤ሕዝ 8፥8:18፤ ዘካ7፥13፤ ሚል2፥13
11፥12 ዘዳ 32፥37: 38፤መሳ10፥14፤ ኤር 44፥17
11፥13 ዘዐ 20፥3፤ 2ነገ17፥29፤ኤር3፥24 ፤7፥9፤19፥4፤ 44፥21
11፥14 ቍ11፤ ዘዐ 32፥10
11፥15 ኤር7፥9-10 ፤ሐጌ2፥12
11፥16 መዝ1፥3፤ ኢሳ27፥11፤ኤር7፥20 ፤21፥14፤ሆሴ 14፥6፤ ሮሜ11፥17-24
11፥17 ቍ11፤ዘዐ 15፥17፤ኢሳ5፥2፤45፥4 ፤ኤር7፥18፤7፥9፤12፥2
11፥19 ቍ21፤ኢዮ 28፥13፤መዝ44፥16 :22፤54፥3፤71፥10፤ 83፥4፤116፥9፤20፥10 ፤ኢሳ53፥8፤ኤር 18፥18

[14]“በተጨነቁ ጊዜ ወደ እኔ ሲጮኹ አልሰማቸውምና አንተም ስለዚህ ሕዝብ አትጸልይ፤ ልመና አታቅርብ፤ አትማጠን::

[15]“ወዳጄ፣ ከብዙዎች ጋር ተንኰሏን እየሸረበች፣
በቤቴ ውስጥ ምን ጒዳይ አላት?
ስእለት ወይም የመሥዋዕት ሥጋ
ቅጣትሽን ሊያስቀርልሽ ይችላልን?
እነዚህንስ በመፈጸም፣ ደስተኛ መሆን
ትችያለሽን?”[ኅ]

[16]*እግዚአብሔር*፣ ‘የተዋበ ፍሬ ያላት፣
የለመለመች የወይራ ዛፍ’ ብሎሽ ነበር፤
አሁን ግን በታላቅ ዐውሎ ነፋስ ድምፅ፣
እሳት ያነድባታል፤
ቅርንጫፎቿ ይሰባበራሉ::

[17]የእስራኤልና የያዕቆብ ቤት ለበኣል በማጠን ባደረጉት ክፋት ስላስቈጡኝ፣ አንቺን የተከለሽ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* ክፉ ነገር ዐውጆብሻል::

## በኤርምያስ ላይ የተደረገ ሤራ

[18]*እግዚአብሔር* ስውር ዕቅዳቸውን ገለጠልኝ፤ እኔም ዐወቅሁ፤ በዚያን ጊዜ ሥራቸውን አሳይቶኝ ነበርና:: [19]እኔም ለመታረድ እንደሚነዳ ጠቦት ነበርሁ፤ እነርሱም፣

“ዛፉን ከፍሬው ጋር እንቍረጥ፤
ከሕያዋን ምድር እናጥፋው፤
ከእንግዲህም ወዲያ ስሙ አይታሰብ::”
ብለው እንዳደሙብኝ ዐላወቅሁም ነበር::
[20]ልብንና ኵላሊትን የምትመረምር፣
በጽድቅም የምትፈርድ የሰራዊት ጌታ
*እግዚአብሔር* ሆይ፤

[ኅ]15 *ወይም ስእለት ወይም የመሥዋዕት ሥጋ ቅጣትሽን ያስቀርልሽ ይችል ይሆን?/ የዚያን ጊዜ ትደሰቻለሽ*

---

እንዲሁም የዘፀ3፥8 ማብ ይመ:: *አሜን፤* በዘዳ27፥15-26 በእያንዳንዱ ቍጥር መጨረሻ ላይ ይገኛል (“... ሰው የተረገመ ይሁን” የሚል ደግሞ በመጀመሪያ ላይ ይገኛል፤ የቍ3 ማብ ይመ):: *የገባሁትን መሐላ እፈጽማለሁ፤* ዘፍ15፥17-18 እና ማብ፤ ዘዳ7፥8 ይመ::

11፥6 *ተናገር፤* 2፥2፤ 3፥12 ይመ::

11፥7 *ደጋግሜ፤* የ7፥13 ማብ ይመ::

*11፥8፤* 7፥24 ይመ:: *የክፉ ልባቸውን እልከኝነት፤* የ3፥17 ማብ ይመ:: *የ ... ኪዳን እርግማን፤* የቍ3 ማብ ይመ:: *ስለዚህ ... አመጣሁባቸው፤* 2ነገ17፥18-23 ይመ::

11፥9 *አድማ፤* ኢዮስያስ ያቀደውን በጎ መንፈሳዊ ለውጥ ለመቃወም ነው (የ1፥2 ማብ ይመ)::

11፥10 *ወዳልፈለጉት፤* ኀጢአታቸው ግልጽ እንቢተኝነት ነበር (የ9፥6 ማብ ይመ):: *ኪዳን፤* የዕብራይስጡ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም “ኪዳኔ” ይላል፤ ይህም የሚያሳየው የኪዳኑ ምንጭ እግዚአብሔር ራሱ መሆኑን ነው::

11፥11 *አመጣባቸዋለሁ፤* እስራኤል ቀደም ሲል የተቀጣችውን ያህል፣ ይሁዳም ትቀጣለች (ቍ10 ይመ፤ እንዲሁም 2ነገ17፥18-23 ይመ)::

11፥12 *ወደሚያጥኑላቸው፤* ቍ13:17 ይመ፤ እንዲሁም የ1፥16 ማብ ይመ::

11፥13 *የአማልክትህ ቍጥር የከተሞችህን ብዛት ያህል ...፤* የ2፥28 ማብ ይመ:: *መሠዊያዎቻችሁ ብዛት የ.... መንገዶች ያህል ... ፤* 2ዜና 28፥24 ይመ:: *አሳፋሪ ለሆነው ጣዖት ለበኣል፤* የዕብራይስጡ አባባል ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “ለነውረኛ ነገር ... ለበኣል” የሚል ነው፤ 3፥24 ይመ፤ እንዲሁም የ2፥26፤ የመሳ6፥32 ማብ ይመ::

11፥14 *ስለዚህ ሕዝብ አትጸልይ፤* የ7፥16 ማብ ይመ፤ ከ1ዮሐ5፥16 ጋር ያነጻጽሩ::

11፥15፤ 7፥10-11:21-24 ይመ:: *ወዳጄ፤* ይሁዳን ለማለት ነው (12፥17 ይመ፤ ብንያም፣ “በእግዚአብሔር የተወደደ” ከተባለበት ከ33፥12 ጋር ያነጻጽሩ)::

11፥16 *‘.... የወይራ ዛፍ’ ብሎሽ ነበር፤* መዝ52፥8፤ 128፥3 ይመ:: *ዐውሎ ነፋስ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ከዚህ ሌላ የሚገኘው የብዙ ሰራዊትን ድምፅ ለማመልከት በሕዝ 1፥24 ላይ ብቻ ነው፤ (ኢሳ13፥4 ይመ):: *ቅርንጫፎቿ ይሰባበራሉ፤* ሕዝ31፥12 ይመ::

*11፥17፤* በዚህ ጥቅስ ላይ የተነገረው የተፈጸመው ይሁዳ በ586 ዓ.ቅ.ክ ስትወድም ነበር (44፥2-3 ይመ):: *ስላስቈጡኝ፤* 8፥19፤ ዘዳ31፥29 ይመ::

*11፥18-23፤* ኤርምያስ ስለ ራሱ በግልጽ ከተናገረባቸው ክፍሎች ይህ የመጀመሪያው ነው::

11፥18 *ዕቅዳቸውን ... ሥራቸውን፤* የኤርምያስ የግል ደመኞች የሆኑትን የወገኖቹን፣ “የዓናቶት ሰዎች” ድርጊት የሚመለከት ነው (ቍ21:23)::

11፥19 *ለመታረድ እንደሚነዳ ጠቦት፤* 51፥40 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ53፥7 እና ማብ ይመ:: *ዛፉን ከፍሬው ጋር እንቍረጥ፤* ከ12፥2 ጋር ያገናዝቡ:: *ከሕያዋን ምድር እናጥፋው፤* ኢሳ53፥8 ይመ፤ ከመዝ27፥13 ጋር ያገናዝቡ:: *ስሙ፤* ኤርምያስ ልጅ ስላልነበረው (16፥2)፣ ስሙ አብሮት ይሞታል:: *ከእንግዲህም ወዲያ ... አይታሰብ፤* ልክ እንደ ክፉ ሰው (ኢዮ24፥20፤ ሕዝ 21፥32 ይመ)::

*11፥20፤* ከ20፥12 ጋር በብዙ ረገድ አንድ ዐይነት አባባል ነው ማለት ይቻላል፤ በተጨማሪም 17፥10 ይመ:: *በጽድቅም*

ጕዳዬን ላንተ ትቻለሁና፤
በእነርሱ ላይ የምትፈጽመውን
በቀል ልይ።

[21]"እንግዲህ ሕይወትህን ለማጥፋት ለሚሹና፣ *'በእግዚአብሔር* ስም ትንቢት አትናገር፤ አለዚያ በእጃችን ትሞታለህ' ለሚሉህ ለዓናቶት ሰዎች *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ [22]ስለዚህ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'እነሆ እኔ እቀጣቸዋለሁ፤ ጕልማሶቻቸው በሰይፍ፣ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውም በራብ ይሞታሉ። [23]በሚቀጡበት ዓመት በዓናቶት ሰዎች ላይ መዓት ስለማመጣ፣ ከእነርሱ የሚተርፍ አንድም አይኖርም።' "

## የኤርምያስ ማጕረምረም

**12** *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ጕዳዬን በፊትህ ሳቀርብ፣
አንተ ጻድቅ መሆንህን እያወቅሁ ነው።
የክፉዎች መንገድ ለምን ይሰምራል?
የከዳተኞችስ ኑሮ ለምን ይሳካል?
[2]አንተ ተክለሃቸዋል፤ ሥርም ሰደዋል፤
አድገዋል፤ ፍሬም አፍርተዋል።
ሁልጊዜ አንተ በአፋቸው ላይ አለህ፤
ከልባቸው ግን ሩቅ ነህ።
[3]ነገር ግን *እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ እኔን
ታውቀኛለህ፤ ታየኛለህ፤
ስለ አንተም ያለኝን ሐሳብ
ትመረምራለህ።
እንደሚታረዱ በጎች ንዳቸው፤
ለዕርድም ቀን ለይተህ አቈያቸው፤
[4]ምድሪቱ በዝናብ እጦት የምትጐዳው፣[a]
የሜዳውም ሣር ሁሉ በድርቅ
የሚመታው እስከ መቼ ነው?
ከነዋሪዎቿ ክፋት የተነሣ፣
እንስሳትና አዕዋፍ ጠፍተዋል፤
ደግሞም ሕዝቡ፣
"በእኛ ላይ የሚሆነውን አያይም"
ብለዋል።

### የእግዚአብሔር ምላሽ

[5]"ከእግረኞች ጋር ሮጠህ፣
እነርሱ ካደከሙህ፣
ከፈረሰኞች ጋር እንዴት ልትወዳደር
ትችላለህ?
በሰላም አገር ከተሰናከልህ፣[b]
በዮርዳኖስ ደን ውስጥ እንዴት ልትሆን
ነው?
[6]ወንድሞችህና የገዛ ቤተ ሰብህ፣
እነርሱ እንኳ አሢረውብሃል፣
በአንተም ላይ ይጮኻሉ፤
በመልካም ቢናገሩህም እንኳ
አትመናቸው።
[7]"ቤቴን እተዋለሁ፤
ርስቴን እጥላለሁ፤
የምወዳትን እርሷን፣
አሳልፌ በጠላቶቿ እጅ እሰጣታለሁ።
[8]ርስቴ፣ በዱር እንዳለ አንበሳ
ተነሥታብኛለች
በእኔም ላይ ጮኻብኛለች፤
ስለዚህ ጠላኋት።

11፥20 1ሳሙ2፥3፤ 1ዜና29፥17፤ መዝ 7፥11፤26፥2፤58፥10፤ ሰቆ3፥60
11፥21 ቍ19፤ ኢሱ 21፥18፤ ኢሳ30፥10፤ ኤር2፥30፤12፥6፤ 18፥23፤21፥7፤26፥8፤ 11፤34፥20፤38፥4
11፥22 ኢሳ9፥17፤ ኤር18፥21
11፥23 ኤር6፥9፤ 23፥12
12፥1 ዕዝ9፥15፤ ኢዮ 5፥8፤8፥3፤ 21፥7፤13፤ መዝ37፥7፤ ኤር5፥27-28፤ ሕዝ18፥25፤ ዳን 9፥14
12፥2 ኢዮ5፥3፤ ኢሳ 29፥13፤ ኤር3፥10፤ 11፥17፤ ሕዝ22፥27፤ ማቴ15፥8፤ ማር7፥6፤ ቲቶ 1፥16
12፥3 መዝ7፥9፤ 11፥5፤44፥11፤139፥1-4፤ ኤር16፥18፤ 17፥18፤ 20፥11
12፥4 ቍ11፤ ዘዳ 28፥15-18፤ ኤር4፥25፤ 26፤28፤52፥10፤ ኢዩ 1፥10-12፤ አሞ1፥2
12፥5 ኤር49፥19፤ 50፥44
12፥6 መዝ12፥2፤ ምሳ26፥24-25፤ ኤር 9፥4
12፥7 2ነገ21፥14፤ ኢሳ5፥1፤ ኤር7፥29፤ 17፥4
12፥8 መዝ17፥12፤ 5፥5፤ ሆሴ9፥15፤ አሞ 6፥8

[a]4 *ወይም ምድሪቱ የምታዝነው*
[b]5 *ወይም በሰላም ምድር ከታመንህ*

---

*የምትፈርድ፤* የዘፍ18፥25 ማብ ይመ።

11፥21 *ሕይወትህን ለማጥፋት ለሚሹና ... ለዓናቶት ሰዎች፤* 12፥6 ይመ፤ "የሰው ጠላቶቹ የቤቱ ሰዎች ናቸው" (ሚክ 7፥6 ጌታ በማቴ10፥36 ላይ የጠቀሰው)።

11፥22 *በሰይፍ ... በራብ፤* የ5፥12 ማብ ይመ።

11፥23 *የሚተርፍ፤* 6፥9፤ ኢሳ10፥20-22 እና ማብ ይመ። *ከእነርሱ፤* ነዋሪዎቿ በሙሉ ሳይሆኑ፣ በዓናቶት የነበሩትን አድመኞች ለማለት ነው፤ ምክንያቱም ከምርኮው በኋላ፣ 128 የዓናቶት ሰዎች ወደ አገራቸው፣ ማለትም ወደ ትውልድ ከተማቸው ተመልሰዋል (ዕዝ2፥23 ይመ)።

*12፥1-6፤* ኤርምያስ ስለ ራሱ በግልጽ ከተናገረባቸው ክፍሎች ይህ ሁለተኛው ሲሆን፣ የመጀመሪያው (11፥18-23) ቅጥያ ነው። ቍ1-4 ላይ የሚናገረው ኤርምያስ ሲሆን፣ በቍ5-6 ላይ እግዚአብሔር መልስ ይሰጣል።

12፥1 *አንተ ጻድቅ መሆንህን እያወቅሁ፤* የዘፍ18፥25 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 11፥20፤ መዝ51፥4፤ ሮሜ3፥4 ይመ። እግዚአብሔር ጻድቅ እንደ መሆኑ መጠን፣ ሊመኩበት የሚገባ የፍትሕ አምላክ ነው። *ይሁን እንጂ፤* እንደዚያም ቢሆን፣ ጥያቄአችንና ብሶታችንን ሊሰማ ዝግጁ ነው። *የክፉዎች መንገድ ለምን ይሰምራል?* ይህ ጥያቄ የኤርምያስ ብቻ አይደለም (ለምሳሌ፦ ኢዮ 21፥7-15፤ ሚል3፥15 ይመ)። እግዚአብሔር በይሁዳ የነበሩ ክፉዎች የኋላ ኋላ እንደሚጠፉ (ቍ7-13)፣ እነርሱንም የሚያጠፉ ክፉ ወራሪዎችም እንደሚጠፉ ይናገራል (ቍ14-17)።

12፥2 *አንተ ተክለሃቸዋል፤* ይሁን እንጂ፣ ልዑል እግዚአብሔር እንደአስፈላጊነቱ ዕቅዱን በመቀየር የልቡን ሐሳብ መፈጸም ይችላል (18፥9-10 ይመ)። *ፍሬም አፍርተዋል፤* የኤርምያስ ወገኖች የገዛ "ፍሬውን" ሊያጠፉበት እያደሙ እያሉ (11፥19 ይመ)፣ ክፉዎች እየለመለሙ ነበር። *በአፋቸው ... ከልባቸው ግን ሩቅ ነህ፤* በከፊልም ቢሆን ጌታ በማቴ15፥8-9 ላይ ጠቅሶታል።

12፥3 *ያለኝን ሐሳብ ትመረምራለህ፤* 11፥20 ይመ። *እንደሚታረዱ በጎች፤* ኤርምያስ በ11፥19 ላይ ለእርሱ የታሰበው ጽዋ በክፉዎቹ የአገሩ ሰዎች ላይ እንዲደርስ ይለምናል። ልመናው ከበቀል የተነሣ ሳይሆን፣ የእግዚአብሔር ፍትሐዊ ትድግና እንዲመጣለት ከመፈለግ የመነጨ ነው።

12፥4 *የምትጐዳው ... በድርቅ የሚመታው፤* 23፥10 ይመ፤ እንዲሁም 3፥3፤ 14፥1 ይመ። በኤርምያስ የአገልግሎት ዘመን በይሁዳ ምድር ተከታታይ ድርቅ የነበረ ይመስላል። *አያይም፤* የነቢዩ ጠላቶች ኤርምያስ የተናገረው ትንቢት እንደሚፈጸሙ አላመኑም ነበር።

*12፥5፤* እግዚአብሔር በኤርምያስ ላይ የሚደርሰው መከራ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየከፋ እንደሚሄድ በመንገር ስለ ወደ ፊቱ ሁኔታ ያስጠነቅቀዋል (ለምሳ 38፥4-6 ይመ)። *ከተሰናከልህ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ብዙ ጊዜ፣ "መታመን" የሚል ትርጕም ያለው ሲሆን፣ በአንዳንድ ስፍራ ባለው አገባቡ አሉታዊነትን ያመለክታል (ለምሳሌ፦ ምሳ14፥16 ይመ)። *ደን፤* የአንበሶች መሸሸጊያና መጠለያ ነው (49፥9፤ 50፥44፤ 11፥3 ይመ)።

12፥6 *ቤተ ሰብህ፤* የዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም "ቤት" ማለት ነው፤ በዚህም መልኩ ከተከታዩ ክፍል (ቍ7) ጋር በድምፅ የተያያዘ ያደርገዋል። የኤርምያስ ቤተ ሰብ ራሱ፣ "የዓናቶት ሰዎች" (11፥21፡23) ከተባሉትና ሊገድሉት ከሚፈልጉት ወገኖች ጋር የተደመረ ይመስላል።

*12፥7-17፤* እግዚአብሔር በይሁዳም ሆነ (ቍ7-13) በአካባቢያቸው በሚገኙት ክፉ ሕዝቦች ላይ (ቍ14-17) ይፈርዳል።

12፥7 *ቤቴን፤* ይሁዳን ማለት ነው (ለምሳሌ፦ 11፥17 ይመ)። *ርስቴን፤* የእግዚአብሔርን ምድርና ሕዝብ ያመለክታል (ቍ8-9፡14-15 ይመ፤ በተጨማሪም ዘፀ15፥17 እና ማብ፤ ዘዳ 4፥20፤ ኢሳ19፥25፤ 47፥6 ይመ)። *የምወዳትን እርሷን፤* የ11፥15 ማብ ይመ።

12፥8 *ጠላኋት፤* "ለጠላቶቿ እጅ አሳልፌ በመስጠት" (ቍ7፤ ሚል1፥3 ይመ)፣ ፍቅሬን አነሣታለሁ ማለት ነው።

[9]ርስቴ ሌሎች አሞሮች፣
ሊበሏት እንደ ከበቧት፣
እንደ ዝንጕርጒር አሞራ አልሆነችምን?
ሂዱ፤ የዱር አራዊትን ሁሉ ሰብስቡ፤
እንዲቀራመቷትም አምጧቸው።
[10]ብዙ እረኞች የወይን ቦታዬን ያጠፋሉ፤
ይዞታዬንም ይረግጣሉ፤
ደስ የምሰኝበትንም ማሳ፣
ጭር ያለ በረሓ ያደርጉታል።
[11]በፊቴ ባድማ፣
ደረቅና ወና ይሆናል፤
መላዪቱም ምድር ጠፍ ትሆናለች፤
ስለ እርሷ የሚገደው የለምና።
[12]በምድረ በዳ ባሉት ወና ኰረብቶች ላይ፣
አጥፊዎች ይሰማራሉ፤
*የእግዚአብሔር* ሰይፍ ከምድር ጫፍ እስከ
ምድር ጫፍ፣
አንዳች ሳያስቀር ይበላል፤
የሚተርፍም የለም።
[13]ስንዴን ይዘራሉ፤ እሾኽን ያጭዳሉ፤
ይደክማሉ፤ የሚያገኙት ግን የለም፤
*ከእግዚአብሔርም* ጽኑ ቍጣ የተነሣ፣
በመኸራችሁ ውጤት ታፍራላችሁ።"

[14]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ለሕዝቤ ለእስራኤል የሰጠሁትን ርስት የሚይዙትን ክፉ ጎረቤቶቼን ሁሉ፣ ከምድራቸው እነቅላቸዋለሁ፤ የይሁዳንም ቤት ከመካከላቸው እነቅላለሁ፤ [15]ከነቀልኋቸው በኋላ ግን መልሼ እምራቸዋለሁ፤ እያንዳንዳቸውንም ወደ ገዛ አገራቸውና ወደ ገዛ ርስታቸው መልሼ አመጣቸዋለሁ፤ [16]የሕዝቤን መንገድ በትጋት ቢማሩና ሕዝቤን በበኣል እንዲምል እንዳስተማሩት ሁሉ፣ 'ሕያው *እግዚአብሔርን*' ብለው በስሜ ቢምሉ፣ በዚያን ጊዜ በሕዝቤ መካከል ይመሠረታሉ፤ [17]የማይሰማኝን ሕዝብ ግን ፈጽሜ እነቅለዋለሁ፤ አጠፋዋለሁም" ይላል *እግዚአብሔር*።

12፥9 ዘዳ28፥26፤ ኢሳ56፥9፤ኤር15፥3፤ሕዝ23፥25፤ 39፥17-20
12፥10 ኢሳ5፥1-7፤ ኤር9፥10፤23፥1፤25፥11፡34፤ሕዝ34፥2-10
12፥11 ቍ4፤ኢሳ 5፥6፤24፥4፤ኤር9፥12፤14፥4፤23፥10
12፥12 ዘዳ32፥41፡42፤ኢሳ31፥8፤ ኤር 3፥2፤7፥10፤46፥10፤47፥6፤ሕዝ 4፥17፤21፥3-4፡28፤33፥2
12፥13 ዘፀ15፥7፤ ዘሌ26፥20፤ዘዳ28፥38፤ኤር4፥26
12፥14 ዘዳ29፥28፤ 28፥63፤2ዜና7፥20፤ መዝ 9፥6፤ዘካ 2፥7-9
12፥15 ዘዳ30፥3፤ መዝ6፥2፤አሞ9፥14-15
12፥16 ኢሱ23፥7፤ ኢሳ26፥18፤49፥6፤ኤር3፥17፤4፥2፤18፥8
12፥17 ዘፍ27፥29
13፥3 ኤር 33፥1
13፥4 ዘፍ 2፥14
13፥5 ዘፀ 40፥16

## ከተልባ እግር የተሠራ መቀነት

**13** *እግዚአብሔር*፣ "ሂደህ ከተልባ እግር የተሠራ መቀነት ግዛ፤ ወገብህንም ታጠቅበት፤ ነገር ግን ውሃ አታስነካው" አለኝ። [2]ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዳዘዘኝ መቀነቱን ገዛሁ፤ ወገቤንም ታጠቅሁበት።

[3]ለሁለተኛም ጊዜ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ፤ [4]"ገዝተህ የታጠቅህበትን መቀነት ይዘህ፣ ወደ ኤፍራጥስ[a] ሂድ፤ በዚያም በዐለት ንቃቃት ውስጥ ሸሽገው።" [5]ስለዚህ *እግዚአብሔር* በነገረኝ መሠረት ወደ ኤፍራጥስ[a] ሄጄ ሸሸግሁት።

[6]ከብዙ ቀን በኋላም *እግዚአብሔር*፣ "ተነሥተህ ወደ ኤፍራጥስ ሂድ፤ በዚያ እንድትሸሽገው የነገርሁህን መቀነት አምጣ" አለኝ። [7]እኔም ወደ ኤፍራጥስ ሄጄ፤ መታጠቂያውን ከሸሸግሁበት ቦታ ቈፍሬ አወጣሁ፤ መታጠቂያውም ተበላሽቶ፣ ከጥቅም ውጭም ሆኖ ነበር።

[8]*የእግዚአብሔርም* ቃል ወደ እኔ እንዲህ

[a]4 ወይም *ፈራት*

12፥9 *ሌሎች አሞሮች ... የዱር አራዊትን፤* የይሁዳን ጠላቶች የሚገልጥ ነው (ኢሳ56፥9 እና ማብ ይመ)።

12፥10 *እረኞች፤* ገዦችን ያመለክታል (የ2፥8 ማብ ይመ)። *የወይን ቦታዬን፤* ይሁዳን ለማለት ነው (2፥21 እና ማብ ይመ)። *ደስ የምሰኝበትንም ማሳ፤* 3፥19 እና ማብ ይመ።

12፥11 *ደረቅ፤* ቍ4 እና ማብ ይመ። በዚህ ቍጥር ላይ ብቻ ሰባት የ"ስ" ድምፅና ሰባት የ"መ" ድምፅ ያላቸው ቃላት በዕብራይስጡ ትርጒም ይገኛሉ፤ ይህም የሚያሳየው ኤርምያስ ምን ያህል ተጠንቅቆ እንደ ጻፈና የሥነ ጽሑፍ ተሰጥኦ እንደ ነበረው ነው።

12፥12 *ወና ኰረብቶች፤* የጣዖት አምልኮ የሚካሄድባቸው ስፍራዎች ነበሩ (3፥2፤ ዘኍ23፥3 ይመ)። *አጥፊዎች፤* ባቢሎናውያንን ነው (የ4፥7 ማብ ይመ)። *የእግዚአብሔር ሰይፍ፤* እግዚአብሔር የመቅጫ መሣሪያ አድርጎ የሚጠቀምበትን ማንኛውንም ነገር የሚያመለክት ነው (25፥29፤ 47፥6 ይመ)። *ከ ... ጫፍ እስከ ... ጫፍ፤* 25፥33 ይመ። *የሚተርፍም የለም፤* ዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ሰላም የሚኖረው አንድም አይገኝም" ይላል (6፥14 እና ማብ ይመ)።

*12፥13፤* 14፥2-4 ይመ።

12፥14 *የሚይዙትን፤* ዕብራይስጡ ቃል በቁሙ ሲተረጐም "የሚነኩትን" ይላል፤ በዘካ2፥8 ላይ ማጥቃትንና መዝረፍን በሚያመለክት መልኩ ሰፍሮ ይገኛል። *ክፉ ጎረቤቶቼ፤* ለምሳሌ:- 2ነገ24፥2 ይመ። *እነቅላቸዋለሁ፤* በምርኮ ተግዘው የሚሄዱ መሆናቸውን ያመለክታል (ለምሳሌ:- 1ነገ14፥15 ይመ)።

*12፥15፤* ከይሁዳ ምድር በምርኮ የተጋዙትና በአጎራባች አገሮች የሚኖሩ አይሁድ በመጨረሻ ላይ ወደየስፍራቸው ተመልሰው ይገባሉ (ቍ16፤32፥37፡44፤33፥26፤48፥47፤49፥6 ይመ)።

*12፥16፤* ኢሳ56፥6-7 ይመ። እዚህ ቍጥር ላይ መሢሑ በምድር ላይ የሚገለጥበት ዘመን ከበስተ ጀርባው ይታያል (ኢሳ2፥2-4 ይመ)። *መንገድ፤* የ10፥2 ማብ ይመ። *ይመሠረታሉ፤* በሚል3፥15 ላይ ይህ ቃል "ጸንተዋል" ተብሎ ተተርጒሞአል።

*13፥1-27፤* በዚህ ምዕራፍ ውስጥ አምስት ተከታታይ ማስጠንቀቂያዎች ተሰጥተዋል፤ የመጀመሪያዎቹ ሁለቱ በስድ ንባብ የተጻፉ ሲሆኑ (ቍ1-11፡12-14)፣ የመጨረሻዎቹ ሦስቱ ደግሞ በግጥም መልክ የቀረቡ ናቸው (ቍ15-17፡18-19፡20-27)።

*13፥1-11፤* የተበላሸውና ከጥቅም ውጭ የሆነውን መቀነት የሚገልጸው ትረካ፣ ኤርምያስ መልእክቱን ለመግለጽ በተግባር እንዲገልጥ እግዚአብሔር ካዘዛቸው ምልክቶች የመጀመሪያውና ትልቁ ነው።

13፥1-2፡4-7 *ሂደህ ... ግዛ፤ ... ገዛሁ፤ ... መቀነት ይዘህ ... ሸሽገው። ተነሥተህ ወደ ኤፍራጥስ ሂድ፤ ... መቀነት አምጣ ...። እኔም ወደ ኤፍራጥስ ሄጄ መታጠቂያውን ... ቈፍሬ አወጣሁ፤* ኤርምያስ እንደ መንፈሳዊ አባቱ እንደ አብርሃም ፈጥኖ የመታዘዝ ባሕርይ ነበረው (ስለ አብርሃም መታዘዝ የዘፍ12፥4 ማብ ይመ)።

13፥1 *ከተልባ እግር፤* የካህናቱም አልባሳት ከዚሁ ዐይነት የተሠሩ ነበሩ (ሕዝ44፥17-18 ይመ)፤ "የመንግሥት ካህናት" የሆኑት የእስራኤል ሕዝብ ቅድስና ምልክት ነው (ዘፀ19፥6 እና ማብ ይመ)። የተልባ እግሩ መቀነት ቀደም ሲል በእግዚአብሔርና በይሁዳ መካከል የነበረው የጠበቀ ግንኙነት ምልክት ነው (ቍ11 ይመ)። *ውሃ አታስነካው፤* አትጠበው ማለት ሲሆን፣ የይሁዳን በኀጢአት የተሞላ ትዕቢት ያመለክታል (ቍ9 ይመ)።

13፥4 *ኤፍራጥስ፤* ምናልባት ኢሱ 18፥23 ላይ፣ "ፋራ" ካለው ጋር አንድ ሊሆን ይችላል፤ ይህም የሚገኘው በአሁኑ ዘመን፣ "ዋዲ ፋራ" ተብሎ ከሚጠራው ከተማ አጠገብ ሲሆን፣ ከአናቶት ሰሜን ምሥራቅ አምስት ኪ.ሜ. ያህል ላይ ነው። ይሁዳ ከአካዝ ዘመን አንሥቶ በአሦራውያንና በባቢሎናውያን ምግባረ ብልሹነት መበከል እንደ ጀመረች ለማሳየት የሚረዳ አንድ ምልክት ነው (2ነገ16 ይመ)።

13፥6 *ከብዙ ቀን በኋላም፤* ምናልባት በባቢሎን የነበረውን የምርኮ ዘመን የሚያሳይ ሳይሆን አይቀርም።

13፥7 *ቈፍሬ አወጣሁ፤* ምናልባት ነቢዩ መቀነቱን ቀብሮት ይሆናል፤ ወይም የሸለቆው ውሃ ደለል አልብሶት ይሆናል። *ተበላሽቶ ... ነበር፤* በዘሌ26፥39 አስቀድሞ እንደ ተገለጸው፣ የእግዚአብሔር ሕዝብ ከኀጢአታቸውና ከአባቶቻቸውም ኀጢአት የተነሣ የተበላሹ ሆነዋል።

ሲል መጣ፤ [9]"*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'የይሁዳን ትዕቢትና የኢየሩሳሌምን እብሪት እንደዚሁ አጠፋለሁ። [10]*ቃሌን* መስማት እምቢ ብለው በልባቸው እልኸኝነት በመሄድ ሊያመልኳቸውና ሊሰግዱላቸው ሌሎችን ጣዖቶች የሚከተሉ እነዚህ ክፉ ሕዝቦች ከጥቅም ውጭ እንደ ሆነው እንደዚህ መቀነት ይበላሻሉ። [11]*መቀነት* በሰው ወገብ ላይ እንደሚታሰር፣ *መ*ላው የእስራኤልና የይሁዳ ቤት ከእኔ ጋር ተጣብቆ ለስሜ ምስጋናና ክብር፣ የኔ ሕዝብ እንዲሆንልኝ አድርጌው ነበር፤ ሕዝቤ ግን አልሰማም' ይላል *እግዚአብሔር*።

## የወይን ጠጅ ማድጋ

[12]"እንዲህ በላቸው፤ 'የእስራኤል ስምባክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ማድጋ ሁሉ በወይን ጠጅ ይሞላል" ይላል። እነርሱም፣ "ማድጋ ሁሉ በወይን ጠጅ እንደሚሞላ እኛ አናውቅምን?" ቢሉህ፣ [13]እንዲህ በላቸው፤ "*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'በዳዊት ዙፋን ላይ የሚቀመጡትን ነገሥታት፣ ካህናትን፣ ነቢያትን እንዲሁም በኢየሩሳሌም የሚኖሩትን ሁሉ ጨምሮ በዚህች ምድር የሚኖሩትን ሁሉ በስካር እሞላቸዋለሁ።' " [14]አንዱን ሰው ከሌላው ጋር፣ አባትንና ወንድ ልጅን እርስ በእርስ አጋጫለሁ፤ ይላል *እግዚአብሔር*፤ ያለ ሐዘኔታ፣ ያለ ምሕረትና ያለ ርኅራኄ አጠፋቸዋለሁ።' "

## የትዕቢት ውጤት

[15]*እግዚአብሔር* ተናግሮአልና፣
ስሙ፤ ልብ በሉ፤
ትዕቢተኞም አትሁኑ።
[16]ጨለማን ሳያመጣ፣
በሚጨልሙትም ተራሮች ላይ፣
እግሮቻችሁ ሳይሰናከሉ፣
በስምባካችሁ *ለእግዚአብሔር* ክብርን ስጡ።
ብርሃንን ተስፋ ታደርጋላችሁ፤
እርሱ ወደ ጨለማ ይለውጠዋል፤
ድቅድቅ ጨለማም ያደርገዋል።
[17]ባትሰሙ ግን፣
ነፍሴ ስለ ትዕቢታችሁ፣
በስውር ታለቅሳለች፤
*የእግዚአብሔር* መንጋ ተማርኮአልና፣
ዐይኔ አምርሮ ያለቅሳል፤
እንባዬም እንደ ጐርፍ ይወርዳል።

[18]ለንጉሡና ለእናቱ ለእቴጌዪቱ፣
የክብር ዘውዳችሁ፣
ከራሳችሁ ይወድቃልና፣
ከዙፋናችሁ ውረዱ" በላቸው።
[19]በኔጌቭ ያሉ ከተሞች ይዘጋሉ፤
የሚከፍታቸውም አይኖርም፤
ይሁዳ ሁሉ ተማርኮ ይሄዳል፤
ሙሉ በሙሉም ይዘጋል።

[20]ዐይኖቻችሁን ከፍታችሁ፣
ከሰሜን የሚመጡትን እዩ።
ለአንቺ የተሰጠው መንጋ፣
የተመካሽባቸው በጎች የት አሉ?
[21]ልዩ ወዳጆች እንዲሆኑሽ
ያስተማርሻቸው፣
ባለ ሥልጣን ሲሆኑብሽ ምን ትያለሽ?
እንደምትወልድ ሴት፣

13፥9 ዘሌ26፥19፤ ማቴ23፥12፤ሉቃ 1፥51
13፥10 መሳ10፥13፤ ዘዳ8፥19፤መክ9፥3፤ ኤር3፥17፤9፥14፤ 22፥21፤ሕዝ 5፥3
13፥11 ዘፀ19፥5-6፤ ኢሳ43፥21፤63፥12፤ 65፥12፤ኤር3፥17፤ 7፥26፤32፥20
13፥13 መዝ60፥3፤ 75፥8፤ኢሳ 9፥9፤ ኤር25፥18፤51፥57
13፥14 ዘዳ29፥20፤ ኢሳ9፥19-21፤ኤር 7፥20፤16፥5፤49፥32፡ 36፤ሰቆ2፥21፤ሕዝ5፥ 10፤7፥4፤8፥18፤9፥5፡ 10፤24፥14፤ዘካ11፥6
13፥15 ዘፀ 23፥21፤ መዝ95፥7-8
13፥16 ዘሌ26፥37፤ ኢሱ7፥19፤ኢዮ3፥5፡ 23፤ ሳሙ2፥9፤መዝ 82፥5፤ኢሳ51፥17፤ ኤር23፥12
13፥17 መዝ80፥1፤ ኤር9፥1፤13፥1፤14፥18 ፤29፥1፤ሚል 2፥2
13፥18 ሳሙ12፥30 ፤1ነገ2፥19፤2ነገ24፥8፤ ኢሳ22፥17፤ኤር21፥ 11፤22፥1፤ሰቆ5፥16፤ ሕዝ16፥12፤21፥26
13፥19 ኤር20፥4፤ 52፥30፤ሰቆ1፥3
13፥20 ኤር6፥22፤ 23፥2፤ዕን1፥6
13፥21 መዝ41፥9፤ ኤር4፥30፡31፤20፥10 ፤38፥22፤አብ1፥7

13፥9 *ትዕቢትና ... እብሪት*፤ ከ9፥23-24 ጋር ያገናዝቡ። ጕራ የተሞላው የይሁዳ ትዕቢት የመውደቂያዋና የመማረኳ ምክንያት ሆኖአል (ቍ15:17 ይመ)፤ ይህም በዘሌ26፥19 አስቀድሞ ተጠቅሶአል።

13፥10 *መስማት እንቢ ብለው*፤ የ9፥6 ማብ ይመ። *በልባቸው እልከኝነት*፤ የ3፥17 ማብ ይመ። *ከጥቅም ውጭ*፤ 24፥8 ይመ።

13፥11 *አልሰማም*፤ ባለመስማታቸውም በዘዳ26፥19 ላይ የተሰጠው የተስፋ ቃል በእነርሱ ሕይወት ተፈጻሚነት አይኖረውም።

*13፥12-14*፤ እግዚአብሔር የይሁዳን መሪዎችና የሕዝቡንም የኋላ ኋላ መጥፋት ለመግለጽ በወይን ጠጅ የተሞሉ ማድጋዎችን ምሳሌ አድርጎ ይጠቀማል።

13፥13 *በስካር*፤ በቁሙ፣ በመጠጥ ይሰክራሉ ለማለት ነው (ለምሳሌ:- ኢሳ28፥7 ይመ)፤ በተጨማሪም የእግዚአብሔርን የቍጣ ወይን ጠጅ ውጤት የሚያመለክት ነው (25፥15-29፤ መዝ60፥3፤ ኢሳ51፥17-20፤ ሕዝ23፥32-34 ይመ)። *ነገሥታትን፣ ካህናትን፣ ነቢያትን ... በኢየሩሳሌም የሚኖሩትን ሁሉ*፤ 26፥16፤ የ1፥18 ማብ ይመ።

13፥14 *አንዱን ሰው ከሌላው ጋር ... አጋጫለሁ*፤ በይሁዳ የሚገኙ የተለያዩ ወገኖች፣ ቈርጠ በመጣባቸው የውጭ ጠላት ላይ የሚያደርጉት ነገር ቢኖር ግራ መጋባትና መታወክ ብቻ ነው። *ያለ ሐዘኔታ፣ ያለ ምሕረትና ያለ ርኅራኄ*፤ 21፥7 ይመ፤ በተጨማሪ ሕዝ5፥11 ይመ።

*13፥15-17*፤ ነቢዩ ኀጢአትን የተሞላ ትዕቢት ጥፋትን እርግዞ እንደሚወልድ ይናገራል።

13፥15 *ስሙ*፤ የ2፥4 ማብ ይመ። *ትዕቢተኞ አትሁኑ*፤ ቍ17 ይመ፤ በተጨማሪም የቍ9 ማብ ይመ።

13፥16 *ለእግዚአብሔር ክብርን ስጡ*፤ ኀጢአታችሁን ተናዘዙ ማለት ነው (ኢሳ7፥19፤ ዮሐ9፥24 ይመ)። *ብርሃንን ተስፋ ታደርጋላችሁ*፤ በአሞ5፥18-20፤ 8፥9 ላይ ከተገለጸው ከጌታ ቀን ጋር ያነጻጽሩ።

13፥17 *ነፍሴ ... ታለቅሳለች*፤ የ9፥1 ማብ ይመ። *ትዕቢታችሁ*፤ ቍ15፤ የቍ9 ማብ ይመ። *መንጋ*፤ ሕዝቡን ለማለት ነው (ቍ20፤ ዘካ10፥3 ይመ፤ በተጨማሪም የ2፥8፤ የ10፥21 ማብ ይመ)። *ተማርኮአልና*፤ በምርኮ ተግዞአል ማለት ነው (ቍ19 ይመ)።

*13፥18-19*፤ በዚህ ክፍል የሚናገረው ነቢዩ ሲሆን፣ በምርኮ የመወሰጃው ሰዓት እጅግ መቃረቡንና አይቀሬ መሆኑን ይገልጻል።

13፥18 *ለንጉሡና ለእናቱ ለእቴጌይቱ*፤ ምናልባት ዮአኪንንና ኔስታን ለመጥቀስ ይሆናል (2ነገ24፥8)። ይህ ከሆነም፣ ዘመኑ ኢዮስያስ ከሞተ ዐሥራ ሁለት ዐመት በኋላ በ597 ዓ.ቅ.ክ ነው ማለት ነው (በ11፥1-13፥27 ላይ የተጻፈውን ማብ ይመ)። *ዘውዳችሁ ... ይወድቃልና*፤ 22፥24-26፤ 29፥2፤ 2ነገ24፥15 ይመ።

13፥19 *በኔጌቭ*፤ በረሐማው የይሁዳ ምድር ክፍል ነው (ዘፍ12፥9 ማብ ይመ)። *ይዘጋሉ*፤ ከቤት ፍርስራሽ ክምችት የተነሣ መተላለፊያ ይጠፋል እንደ ማለት ነው (ኢሳ24፥10 ይመ)። *ሙሉ በሙሉ ይዘጋል*፤ አሞ1፥6:9 ይመ።

*13፥20-27*፤ በመጀመሪያ ነቢዩ (ቍ20-23)፣ ከዚያም እግዚአብሔር ይናገራል (ቍ24-27)። ይሁዳ ሆን ብላ በማመፅዋ በምርኮ መወሰዷ የማይቀር ሆኖአል።

13፥20 *ከሰሜን*፤ ከባቢሎን ምድር ለማለት ነው (4፥6 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ41፥25 ማብ ይመ)። *ለአንቺ*፤ ኢየሩሳሌምን በሴት አስመስሎ በሰውኛ አነጋገር ሲያመለክት ነው (ቍ21-22:26:27 ይመ)፤ መልእክቱ የሚተላለፈውም ለኢየሩሳሌም ነው። *መንጋ ... በጎች*፤ የቍ17 ማብ ይመ።

13፥21 *ልዩ ወዳጆች*፤ ምናልባት ይሁዳን ተራ በተራ ይዘዋት የነበሩ ግብፅና ባቢሎን ይሆናሉ። *እንደምትወልድ ሴት*፤

ምጥ አይዝሽምን?
[22]"ይህ ለምን ደረሰብኝ' " ብለሽ
ራስሽን ብትጠይቂ፣
ልብስሽን ተገልበሽ የተገፈተርሽው፣
በሰውም እጅ የተንገላታሽው፣
ከኀጢአትሽ ብዛት የተነሣ ነው::
[23]ኢትዮጵያዊ* መልኩን፣
ነብርስ ዝንጕርጕርነቱን መለወጥ
ይችላልን?
እናንተ ክፉ ማድረግ የለመዳችሁትም፣
መልካም ማድረግ አትችሉም::

[24]"የበረሓ ነፋስ ብትንትኑን
እንደሚያወጣው ገለባ፣
እንዲሁ እበታትናችኋለሁ::
[25]እኔን ረስተሽ፣
በከንቱ አማልክት ስለታመንሽ፣
ያወጅሁልሽ ድርሻሽ፣
ዕጣ ፈንታሽ ይህ ነው፤"
ይላል *እግዚአብሔር*፤
[26]"ኀፍረትሽ እንዲገለጥ፣
ልብስሽን ፊትሽ ድረስ እገልባለሁ፤
[27]በኰረብቶችና በሜዳዎች ላይ፣
አስጸያፊ፣ ተግባርሽን፣
ምንዝርናሽንና ማሽካካትሽን፣
ኀፍረተቢስ ግልሙትናሽን አይቻለሁ::
ኢየሩሳሌም ሆይ፤ ወዮልሽ፤
ከርኵሰትሽ የማትጸጂው እስከ መቼ
ነው' "

## ድርቅ፣ ራብ፣ ሰይፍ

**14** ስለ ድርቅ ወደ ኤርምያስ የመጣው *የእግዚአብሔር* ቃል ይህ ነው፤

[2]"ይሁዳ ታለቅሳለች፤
ከተሞቿም ይማቅቃሉ፤
በምድር ላይ ተቀምጠው ይቈዝማሉ፤
ጩኸትም ከኢየሩሳሌም ወጥቶ
ይሰማል::
[3]መሳፍንት አገልጋዮቻቸውን ውሃ ፍለጋ
ይሰዳሉ፤
እነርሱ ወደ ውሃ ጕድጓዶች ይወርዳሉ፤
ነገር ግን ውሃ አያገኙም፤
ዐፍረውና ተስፋ ቈርጠው፣
ራሳቸውን ተከናንበው፣
ባዶ እንስራ ይዘው ይመለሳሉ::
[4]በምድሪቱ ዝናብ ስለ ሌለ፣
መሬቱ ተሰነጣጥቆአል፤
ገበሬዎችም ዐፍረው፣
ራሳቸውን ተከናንበዋል::
[5]አንዳች ሣር ባለመኖሩ፣
የሜዳ አጋዘን እንኳ፣
እንደ ወለደች ግልገሏን ጥላ ትሄዳለች::
[6]የሜዳ አህዮች ባድማ ኰረብቶች ላይ
ቆሙ፤
እንደ ቀበሮም አየር ፍለጋ አለከለኩ፤
ግጦሽ ባለመገኘቱ፣
ዐይኖቻቸው ፈዘዙ::"
[7]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከአንተ መኰብለል
አብዝተናል፤
በአንተም ላይ ዐምፀናል፤
ኀጢአታችን ቢመሰክርብንም እንኳ፣
ስለ ስምህ ብለህ አንድ ነገር
አድርግልን::
[8]አንተ የእስራኤል ተስፋ፤
በጭንቀት ጊዜ አዳኙ፣
ለምን በምድሪቱ እንደ ባዕድ፣
እንደ ሌት አዳሪ መንገደኛ ትሆናለህ?
[9]ግራ እንደ ተጋባ ሰው፣
ለመታደግም ኀይል እንዳጣ ተዋጊ
ትሆናለህ?

*23 ዕብራይስጡ *ኩሻዊ* ይላል (ምናልባት በላይኛው ዐባይ አካባቢ ይሚኖር ሰው ሊሆን ይችላል)::

13፥22 1ነገ9፥9፤ ኢሳ20፥1፤ኤር9፥2-6፡ 16:10-12፤ሰቆ1፥8 ፤ሕዝ16፥37፤23፥26፤ ናሆ3፥5-6
13፥23 2ዜና6፥36
13፥24 ዘሌ26፥33፤ ኢዮ1፥19፤27፥21፤ መዝ1፥4
13፥25 ዘዳ31፥20፤ ኢዮ20፥29፤መዝ4፥2 ፤106፥19-21፤ኢሳ 17፥10፤ማቴ 24፥51
13፥26 ሰቆ1፥8፤ ሕዝ16፥37፤ናሆ3፥5
13፥27 ኢሳ57፥7 ፤ሕዝ6፥13፤23፥29፤ ሆሴ8፥5
14፥1 ዘዳ28፥22፤ ኢሳ5፥6
14፥2 ኢሳ3፥26
14፥3 ዘዳ28፥48፤ 2ነገ 18፥31፤ አስ 6፥12፤ኢዮ6፥19-20
14፥4 ኤር3፥3፤ 12፥11፤አሞ 4፥8፤ ዘካ14፥7
14፥5 ኢሳ15፥6
14፥6 ዘፍ47፥4፤ኢዮ 39፥5-6፤መዝ104፥11 ፤ ኤር2፥24
14፥7 1ሳሙ12፥22 ፤መዝ79፥9፤ኢሳ3፥9 ፤ኤር2፥19፤5፥6፤ 8፥14፤ሆሴ5፥5
14፥8 መዝ9፥18፤ 18፥46፤46፥1ኢሳ 25፥9፤ ኤር 17፥13፤ 50፥7
14፥9 ዘፍ17፥7፤ መዝ27፥9፤ኢሳ50፥2 ፤63፥19፤ኤር8፥19፤ 15፥16

6፥24፤ 49፥24፤ 50፥43 ይመ::

13፥22 *ልብስሽን ተገልበሽ የተገፈተርሽው*፤ እንደ ዝሙት አዳሪ በሕዝብ ፊት የተዋረደች ማለት ነው (ቍ26-27፤ ኢሳ47፥3፤ ሆሴ2፥3:10 ይመ)::

*13፥23፤* ጥያቄው መልስ የሚጠብቅ አይደለም፤ ምላሹ አሉታዊ መሆኑ የታወቀ ነውና (17፥9 ይመ)::

13፥24 *ነፋስ ብትንትኑን እንደሚያወጣው ገለባ፤* የክፉዎች መጨረሻ ይኸው ነው (ለምሳሌ:- መዝ1፥4 ይመ):: *የበረሓ ነፋስ፤* የ4፥11 ማብ ይመ::

13፥25 *እኔን ረስተሽ፤* የ2፥32 ማብ ይመ::

*13፥26፤* ቍ22 እና ማብ ይመ::

13፥27 *ምንዝርናሽንና ማሽካካትሽን፤* የ5፥8 ማብ ይመ:: *ኀፍረተ ቢስ ግልሙትናሽን፤* ሕዝ16፥27 ይመ:: *እስከ መቼ ... ?* የእግዚአብሔርን ቍጣ የማሳለፍ ዕድል እጅግ የመነመነ ቢሆንም፣ አሁንም ተስፋ አለ (ለምሳሌ:- ከ12፥14-16 ጋር ያነጻጽሩ)::

*14፥1-15፥21፤* ኤርምያስ በዚህ ክፍል የሚገኘውን መልእክት ያስተላለፈው በከባድ የድርቅ ወራት እንደ ነበር ይታወቃል፤ ሆኖም ድርቁ የተከሠተበት ወቅት ወይም ዘመን አይታወቅም::

*14፥1-15፥9፤* ኤርምያስ ስለ ድርቁ ሁኔታ በመጀመሪያ በዝርዝር ከገለጸ በኋላ (14፥2-6)፣ ጣልቃ እያስገባ ይጸልያል (14፥7-9:13:19-22)፤ እግዚአብሔርም ምላሽ ይሰጣል (14፥10-12:14-18፤ 15፥1-9)::

14፥1 *ድርቅ*፤ 17፥8 ይመ:: 3፥3፤ 12፥4 እንደ ተገለጸው ሳይሆን፣ እዚህ ላይ ጠላት አገሪቱን ስለ ወረረ መከራው እያየለ ሄዶአል (ቍ18 ይመ)፤ ድርቅ እርግማን ያስከትላሉ ተብለው ከሚፈሩት አንዱ ነበር (23፥10 ይመ)፤ ይህም የሚደርሰው ከእግዚአብሔር ጋር ያደረጉትን ቃል ኪዳን አፍርሰው ሲገኙ ነበር (ዘሌ26፥19-20፤ ዘዳ28፥22-24 ይመ)::

14፥2 *ከተሞቿም*፤ ዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ደጆቿ" ይላል (የዘፍ22፥17 ይመ)፤ 15፥17 ይመ::

14፥3 *መሳፍንት*፤ ድርቅ እገሌ ከእገሌ፣ ሀብታም ከድኻ ሳይል፣ ሁሉንም በአንድነት ይመታል:: ራሳቸውን *ተከናንበው፤* የሐዘን ምልክት ነው (ቍ4፤ 2ሳሙ15፥30 ይመ፤ ከ2ሳሙ19፥4 ጋር ያነጻጽሩ)::

14፥4 *ዝናብ ስለ ሌለ*፤ 1ነገ17፥7 ይመ:: በታላቁ ዐባይ ወንዝ ምድሩ እንደሚርሰለት እንደ ግብፅ ሳይሆን፣ የመካከለኛ ምሥራቅ አገሮች ውሃ የሚያገኙት በአብዛኛው ከዝናብ ብቻ ነው::

14፥6 *አለከለኩ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በ2፥24 ላይ፣ "ማነፍነፍ" ተብሎ ተተርጕሞአል:: በዚያኛው አገባቡ ሴቲቱ አህያ (ኢየሩሳሌም) ወንዱን በእጅጉ የፈለገችበትን ወቅት የሚገልጽ ሲሆን፣ እዚህኛው ላይ ግን ወንዱ የሜዳ አህያ በይሁዳ ኀጢአት በመጣው ድርቅ የተነሣ ውሃ ጠምቶት እያለከለከ መሆኑን የሚገልጥ ነው::

*14፥7-9፤* ነቢዩ ስለ ሕዝቡ ይጸልያል (ቍ11 ይመ)::

14፥7 *ስለ ስምህ ብለህ*፤ ቍ21፤ ኢሱ7፥9፤ ኢሳ48፥9-11 ይመ:: *መኰብለል አብዝተናል*፤ 2፥19፤ 3፥22፤ 5፥6 ይመ:: ቃሉ ክህደትን ጭምር የሚያመለክት ነው::

14፥8 *አንተ የእስራኤል ተስፋ*፤ ቍ22፤ 17፥13፤50፥7፤ሐሥ 28፥20 ይመ::

14፥9 *በስምህም ተጠርተናል*፤ ምን ጊዜም ታዳጊያችን

*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ በመካከላችን
 አለህ፤
 በስምህም ተጠርተናል፤
 እባክህ አትተወን።

[10] *እግዚአብሔር* ስለዚህ ሕዝብ እንዲህ ይላል፤

"መቅበዝበዝ እጅግ ይወዳሉ፤
 እግሮቻቸው አይገቱም፤
 ስለዚህ *እግዚአብሔር* በእነርሱ ደስ
 አይለውም፤
 አሁን በደላቸውን ያስባል፤
 በኀጢአታቸውም ይቀጣቸዋል።"

[11] *እግዚአብሔርም* እንዲህ አለኝ፤ "ለዚህ ሕዝብ በጎነት አትጸልይ፤ [12] ቢጾሙም ጩኸታቸውን አልሰማም፤ የሚቃጠል መሥዋዕትና የእህል ቍርባን ቢያቀርቡም አልቀበላቸውም፤ ነገር ግን በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር አጠፋቸዋለሁ።"

[13] እኔም፣ "ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ወዮ! ነቢያቱ 'ሰይፍ አታዩም፤ ራብም አያገኛችሁም፤ ነገር ግን በዚህ ስፍራ ዘለቄታ ያለው ሰላም እሰጣችኋለሁ' ይላል ይሏቸዋል" አልሁ።

[14] *እግዚአብሔርም* እንዲህ አለኝ፤ "ነቢያቱ በስሜ የሐሰት ትንቢት[a] ይናገራሉ፤ እኔ አልላክኋቸውም፤ አላዘዝኋቸውም፤ አልተናገርኋቸውምም። የሐሰት ራእይ፣ ሟርት፣ ከንቱ ነገርንና የልባቸውን ሽንገላ ይተነብዩላችኋል። [15] ስለዚህ በስሜ የሐሰት ትንቢት ስለሚናገሩ ነቢያት *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ እኔ ሳልልካቸው፣ 'ሰይፍና ራብ በዚች ምድር ላይ አይመጣም' የሚሉ እነዚህ ነቢያት በሰይፍና በራብ ይጠፋሉ፤ [16] ትንቢቱ የተነገረለትም ሕዝብ ከሰይፍና ከራብ የተነሣ በኢየሩሳሌም አደባባዮች ይወድቃል፤ እነርሱንም ሆነ ሚስቶቻቸውን ወይም ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን የሚቀብራቸው አይገኝም። በደላቸው የሚገባውንም ቅጣት በላያቸው አወርዳለሁ።

[17] "ይህን ቃል እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤
" 'ድንግሊቱ ልጄ፣ ሕዝቤ፣
 በታላቅ ስብራት፣
በብርቱ ቍስል ተመትታለችና
 ዐይኖቼ ቀንና ሌሊት፣ ሳያቋርጡ
 እንባ ያፈስሳሉ።
[18] ወደ ገጠር ብወጣ፣
 በሰይፍ የተገደሉትን አያለሁ፤
ወደ ከተማ ብገባ፣ በራብ የወደቁትን
 አያለሁ።
 ነቢዩም ካህኑም፣
 ወደማያውቁት አገር ሸሽተዋል።' "

[19] ይሁዳን ፈጽመህ ጥለኸዋልን?
 ነፍስህስ ጽዮንን ተጸየፈቻትን?
ፈውስ እስከማይገኝልን ድረስ፣
 ለምን ክፉኛ መታኸን?
ሰላምን ተስፋ አደረግን፤
 ሆኖም በጎ ነገር አላገኘንም፤
የፈውስን ጊዜ ተጠባበቅን፤
 ነገር ግን ሽብር ብቻ ሆነ።
[20] *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ክፋታችንን
 ዐውቀናል፤
 የአባቶቻችንን በደል ተረድተናል፤
 በእርግጥም በአንተ ላይ ኀጢአት
 ሠርተናል።
[21] ስለ ስምህ ብለህ አትናቀን፤
 የክብርህንም ዙፋን አታዋርድ።
ከእኛ ጋር የገባኸውን ኪዳን አስብ፤
 አታፍርሰውም።
[22] ከአሕዛብ ከንቱ ጣዖቶች መካከል ዝናብ
 ሊያዘንብ የሚችል አለን?
 ሰማያትስ በራሳቸው ማካፋት ይችላሉን?
አይ! አይችሉም፣ *እግዚአብሔር* አምላካችን
 ሆይ፤

[a]14 ወይም ራእይ፣ (ከንቱ) ሟርት

14፥10 መዝ119፥101፤ኤር2፥25፤6፥20፤44፥21-23፤ሆሴ7፥2፤8፥13፤9፥9፤አሞ3፥2፤5፥22፤8፥7
14፥11 ዘፀ32፥10፤1ሳሙ2፥25
14፥12 ዘሌ1፥1-17፤2፥1-16፤ዘዳ1፥45፤1ሳሙ8፥18፤ኢሳ 51፥19፤ኤር7፥21፤9፥16፤11፥11፤15፥2፤16፥4፤21፥6፤27፥8፡13፤32፥24፤34፥17፤ሕዝ14፥21፤አሞ5፥22
14፥13 ዘዳ 18፥22፤ኢሳ30፥10፤ኤር4፥10፤5፥12፤27፥14፤37፥19
14፥14 ኤር5፥1፤23፥16፡21፡25፡32፤27፥14፤29፥31፤ሰቆ2፥9፤ሕዝ12፥24፤13፥2፡6
14፥15 ኤር5፥12-13፤16፥4፤20፥6፤ሰቆ1፥19፤ሕዝ14፥9
14፥16 መዝ79፥3፤ምሳ1፥31፤ኤር7፥33፤17፥10
14፥17 2ነገ19፥21፤መዝ119፥136፤ኢሳ23፥12፤ኤር8፥21
14፥18 2ዜና36፥10፤ኤር 13፥17፤ ሕዝ7፥15
14፥19 ኢዮ19፥8፤ኢሳ1፥6፤ኤር7፥29፤8፥15፤ 30፥12-13
14፥20 ዘሌ 26፥40፤መሳ10፥10፤1ነገ 8፥47፤ዕዝ9፥6፤ኤር3፥13፤ዳን9፥7-8
14፥21 ቍ7፤ዘፀ2፥24፤ኢሱ7፥9፤ኢሳ62፥7፤ኤር3፥17
14፥22 1ነገ8፥36፤መዝ135፥7፤ኢሳ41፥24፤43፥10፤44፥10፤ኤር10፥15፤16፥19፤ዕን2፥18

ነህ፣ የአንተ ገንዘብ ነን ማለት ነው (የ7፥10 ማብ ይመ)።

*14፥10-12፤* እዚህ ላይ መልስ የሚሰጠው እግዚአብሔር ነው።

14፥10-11 *ስለዚህ ሕዝብ፤* እዚህ ላይ እግዚአብሔር እንደ ራሱ ሕዝብ አድርጎ አይቀበላቸውም (ኢሳ6፥9-10፤ 8፥6፡11-12 ይመ)።

14፥10 *መቅበዝበዝ፤* ሐሰተኛ አማልክትን በመከተል (2፥23፡31 ይመ)። *እግዚአብሔር... ይቀጣቸዋል፤* ለእነዚህ ሦስት መስመሮች (ስንኞች) የገባው የዕብራይስጡ አባባል፣ ቃል በቃል ከሆሴ8፥13 የተወሰደ ነው (ከሆሴ9፥9 ጋር ያነጻጽሩ)።

14፥11 *አትጸልይ፤* የ7፥16 ማብ ይመ። ከ1ሳሙ7፥8፤ 12፥9 ጋር ያነጻጽሩ።

14፥12 *አልቀበላቸውም፤* ቍ10 ይመ። ንስሓ ሳይገቡ መሥዋዕት ማቅረብ ከንቱ ልፋት ነው (የ6፥20 ማብ ይመ)። *በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር፤* የእግዚአብሔርን ኪዳን ከማፍረስ የተነሣ የሚደርሱ እርግማኖች ናቸው (ዘሌ26፥25-26 ይመ)፤ እነዚህ በጥምረት የተጠቀሱት ሦስት ቃላት በትንቢተ ኤርምያስ ውስጥ ዐሥራ አምስት ጊዜ በአንድነት የተጠቀሱ ሲሆን፣ እዚህ ላይ ለመጀመሪያ ጊዜ መጠቀሳቸው ነው።

*14፥13፤* ሐሰተኛ ነቢያት የሚናገሩትን ኤርምያስ ለእግዚአብሔር ይገልጣል። *ሰይፍ አታዩም፤ ራብም አያገኛችሁም፤* 5፥12 ይመ። *ዘለቄታ ያለው ሰላም፤* ሐሰተኛ ነቢያት "ሰላም፣ ሰላም" ያሉትን (6፥14፤ 8፥11 ይመ) ኤርምያስ በዚህ መልክ አቅርቦታል።

*14፥14-18፤* እግዚአብሔር እየተናገረ ነው።

14፥14 *የሐሰት፤* 5፥12 ይመ። በስሜ፤ ዘዳ 18፥20፡22 ይመ። *የልባቸውን ሽንገላ፤* 23፥26 ይመ።

14፥15 *እነዚህ ነቢያት ... ይጠፋሉ፤* 28፥15-17፤ ዘዳ 18፥20 ይመ።

14፥16 *የሚቀብራቸው አይገኝም፤* የ7፥33 ማብ ይመ። *ሚስቶቻቸውን ... ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን፤* ሁሉም ለጣዖታት ሰግደዋልና ሁሉም ይጠፋሉ (የ7፥18 ማብ ይመ)።

14፥17 *ድንግሊቱ ልጄ፤* በኢሳ37፥22 ላይ ስለ ኢየሩሳሌም በተመሳሳይ አባባል ተጠቅሶአል (የተጠቀሰውን ቍጥር ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ23፥12 እና ማብ ይመ)፤ 18፥13 ይመ። *ዐይኖቼ ... ሳያቋርጡ እንባ ያፈሳሉ፤* 9፥18፤ 13፥17 ይመ።

*14፥19-22፤* ነቢዩ እዚህ ላይ ስለ ሕዝቡ ይጸልያል።

14፥20 *የአባቶቻችንም በደል፤* 2፥5-6፤ 7፥25-26 ይመ። *ኀጢአት ሠርተናል፤* ንስሐ መግባት ከቅጣት ያድናል፤ ወደ ነበሩበት በጎ ሁኔታ ለመመለስም ይረዳል (ዘዳ30፥2-3 ይመ)።

14፥21 *የክብርህንም ዙፋን፤* በኢየሩሳሌም የነበረውን ቤተ መቅደስ የሚያመለክት ነው (17፥12፤ 2ነገ19፥14-15፤ መዝ99፥1-2 ይመ)። *የገባኸውን ኪዳን አስብ ... አታፍርሰውም፤* ኤርምያስ ወደ እግዚአብሔር ልመና የሚያቀርበው እግዚአብሔር በዘሌ26፥44-45 ላይ የገባውን ቃል ኪዳን መሠረት በማድረግ ነው።

*14፥22፤* ሆሴ2፥8፡21-22 ይመ። *ከንቱ ጣዖቶች፤* የ2፥5 ማብ ይመ። አንተ ብቻ ነህ፤ ምድሪቱ ከደረሰባት ድርቅ (ቍ1

ይህን ሁሉ የምታደርግ አንተ ነህ፣
ስለዚህም ተስፋችን በአንተ ላይ ነው።

**15** እግዚአብሔርም እንዲህ አለኝ፤ "ሙሴና ሳሙኤል እንኳ በፊቴ ቢቆሙ፣ ልቤ ለዚህ ሕዝብ አይራራምና፤ ከፊቴ አስወጣቸው፤ ይሂዱ። [2]እነርሱም፣ 'ወዴት እንሂድ?' ቢሉህ፣ እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ 'እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

" 'ለሞት የተመደበ ወደ ሞት፣
ለሰይፍ የተመደበ ወደ ሰይፍ፣
ለራብ የተመደበ ወደ ራብ፣
ለምርኮ የተመደበ ወደ ምርኮ ይሄዳል።'

[3]"እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'አራት ዐይነት አጥፊዎችን እሰድባቸዋለሁ፤ እነዚህም፦ ለመግደል ሰይፍ፣ ለመጐተት ውሾች፣ እንዲሁም ጠራርጎ ለመብላትና ለማጥፋት የሰማይ ወፎችና የምድር አራዊት ናቸው። [4]የይሁዳ ንጉሥ የሕዝቅያስ ልጅ ምናሴ በኢየሩሳሌም ካደረገው በደል የተነሣ፣ ለምድር ነገሥታት ሁሉ መሰቀቂያ አደርጋቸዋለሁ።

[5]"ኢየሩሳሌም ሆይ፤ የሚራራልሽ ማን ነው?
ማንስ ያለቅስልሻል?
ደኅንነትሽንስ ማን ጎራ ብሎ ይጠይቃል?
[6]እኔን ጥለሸኛል" ይላል እግዚአብሔር፤
"ወደ ኋላም እያፈገፈግሽ ነው፤
ስለዚህ እጄን በአንቺ ላይ አነሣለሁ፤
አጠፋሻለሁም፤
ከእንግዲህም አልራራልሽም።
[7]በአገሪቱ የከተማ ደጆች፣
በመንሽ እበትናቸዋለሁ፤
ከመንገዳቸው አልተመለሱምና፣
ሕዝቤን በሐዘን እመታለሁ፤
ጥፋትም አመጣባቸዋለሁ፤
[8]የመበለቶቻቸውን ቍጥር፣
ከባሕር አሸዋ ይልቅ አበዛለሁ፤
ይጐበዛዝት እናቶች በሆኑትም ላይ፣
አጥፊውን በቀትር አመጣባቸዋለሁ።
ሽብርንና ድንጋጤን፣
በድንገት አወርድባቸዋለሁ።
[9]የሰባቶቹ እናት ትዝለፈለፋለች፤
ትንፋሿም ይጠፋል፤
ገና ቀን ሳለ ፀሐይዋ ትጠልቃለች፤
እርሷም ታፍራለች፤ ትዋረዳለችም፤
የተረፉትንም በጠላቶቻቸው ፊት፣
ለሰይፍ እዳርጋቸዋለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር።

[10]ወይኔ እናቴ! ለምድር ሁሉ፣
የጭቅጭቅና የክርክር ሰው የሆንሁትን
ምነው ወለድሽኝ!
ለማንም አላበደርሁም፤ ከማንም
አልተበደርሁም፤
ነገር ግን ሰው ሁሉ ይረግመኛል።

15፥1 ዘፀ32፥11፤ ዘኍ14፥13-20፤1ሳሙ 1፥20፤7፥8፤1ሳሙ 2፥25፤2ነገ17፥20፤ ኤር7፥16፤16፥13
15፥2 ዘዳ28፥26፤ ኤር14፥12፤42፥22፤ 43፥11፤44፥13፤ሰቆ 4፥9፤ሕዝ12፥11፤ራእ 13፥10
15፥3 ዘሌ26፥22፡ 25፤ዘኍ33፥4፤ዘዳ28፥ 26፤1ነገ21፥19፤2ነገ 9፥36፤ሕዝ14፥21፤ 33፥27
15፥4 ዘዳ 28፥25፤ 2ነገ21፥2፤23፥26-27፤ ኢዮ17፥6፤ኤር24፥9፤ 29፥18፤34፥17
15፥5 ኢሳ27፥11፤ 51፥19፤ኤር13፥14፤ 16፥13፤21፥7፤ናሆ 3፥7
15፥6 ዘዳ32፥15፤ኢ ሳ31፥3፤ኤር6፥19፤7፥ 20፤አሞ7፥8፤ሰፎ1፥4
15፥7 2ዜና28፥22፤ ኢሳ41፥16፤3፥26፤ ኤር18፥21
15፥8 ኢዮ18፥11፤ ኢሳ47፥9፤ኤር4፥7፤ 6፥4
15፥9 1ሳሙ2፥5፤ 2ነገ25፥7፤ኢዮ8፥13፤ ኤር7፥19፤19፥7፤21፥ 7፤25፥31
15፥10 ዘሌ25፥36፤ ነህ5፥1-12፤ኢዮ3፥11 10፥18-19፤ኤር1፥19፤ 6፥10

ይመ) ነጻ ትሆን ዘንድ ዝናብ ማዝነብ የሚችለው እግዚአብሔር ብቻ ነው። *ተስፋችን በአንተ ላይ ነው*፤ የቍ8 ማብ ይመ።

*15፥1-9፤* በዚህ ክፍል የሚገኘው ሐሳብ የእግዚአብሔር አጠቃላይ ምላሽ ነው (የ14፥1-15፥9 ማብ ይመ)።

15፥1 *ሙሴና ሳሙኤል*፤ ሁለቱ ስለ በደለኛዋ እስራኤል በመማለድ የታወቁ ነቢያት ነበሩ (ዘፀ32፥11-14፡30-34፤ መዝ99፥6-8 ይመ)። *በፊቴ ቢቆሙ*፤ የእግዚአብሔር አገልጋዮች ሲጸልዩ በእግዚአብሔር ፊት ያላቸውን የአቋቋም ሁኔታ ያሳያል (ዘፍ18፥22 ይመ)። *ከፊቴ አስወጣቸው*፤ ሕዝቡ እጅግ ዐመፀኞች በመሆናቸው፣ ስለ እነርሱ ወይም በእነርሱ የሚቀርበውን ጸሎት እግዚአብሔር ሊሰማ ፈቃደኛ አልነበረም። የእግዚአብሔርን ምሕረት ማግኘት ከማይችሉበት ደረጃ ላይ ደርሰዋል (የ7፥16፤ የ14፥11-12 ማብ ይመ)።

*15፥2፤* ሕዝ14፥21፤ 33፥27 ይመ። *ሞት*፤ በመቅሠፍት አማካይነት የሚመጣ ሞት ሊሆን ይችላል፤ 14፥12 (እና ማብ ይመ፤ በዚህ ክፍል እግዚአብሔር ሕዝቡን የሚቀጣባቸው ሦስቱ ነገሮች "ሰይፍ፣ ራብና ቸነፈር" አብረው ተጠቅሰዋል።

*15፥3-4፤* በዘዳ28፥25-26 ላይ አስቀድሞ የተገለጸ ሐሳብ አለው።

15፥3 *አራት ዐይነት*፤ ቍ2 ላይ የተጠቀሱትን አራት ነገሮችን ሳይሆን፣ በሰይፍ የተገደሉትን ሰዎችን ሬሳዎች ከሚያጋጥሙ የወደፊት አስከፊ ዕጣ ፈንታዎች ውስጥ የሦስቱን ማብራሪያ የሚያሳይ ነው። *ውሾች፤* 1ነገ21፥23 ይመ። *የምድር አራዊት*፤ ራእ6፥8 ይመ።

15፥4 *መሰቀቂያ*፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በዘዳ28፥25 ላይ "ማስደንገጫ ነገር" ተብሎ ተተርጕሞአል። *ምናሴ በኢየሩሳሌም ካደረገው*፤ ቅን የነበረው የንጉሡ የኢዮስያስ አያት፣ ምናሴ በይሁዳ ሕዝብ ረዥም ታሪክ ውስጥ እጅግ ክፉ ንጉሥ ነበር (2ነገ21፥1-11፡16 ይመ)። ይሁዳን የኋላ ኋላ እንድትጠፋ ያደረገው የእርሱ ኀጢአት ነበር (2ነገ21፥12-15፤ 23፥26-27፤ 24፥3-4 ይመ)።

*15፥5-9፤* በ586 ዓ.ቅ.ክ በኢየሩሳሌም ላይ ስለሚደርሰው ጥፋት የተጻፈ ግጥም ነው (ሰቆ1፥1፡12፡21፤ 2፥13፡20 ይመ)።

*15፥5፤* ከማቴ23፥37 ጋር ያነጻጽሩ።

15፥6 *ወደ ኋላም እያፈገፈግሽ ነው*፤ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ወደ ኋላ እየሄድሽ ነው" የሚል ትርጕም አለው (ከ7፥24 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ2፥19 ማብ ይመ)።

15፥7 *በመንሽ እበትናቸዋለሁ*፤ የሩት1፥22 ማብ ይመ። በመንሽ እህልን ከገለባ ማጥራት የፍርድ ማስፈጸሚያ ምሳሌ ሆኖ በተጨማሪ በ51፥2፤ በምሳ20፥8፡26፤ በኢሳ41፥16 ጥቅም ላይ ውሎ ይገኛል። *በአገሪቱ የከተማ ደጆች*፤ በቀላሉ "የአገሪቱ ደጆች" ማለትም ይቻላል (ይኸውም በናሆ3፥13 እንደ ተገለጸው ማለት ነው)፤ ወደ አገሪቱ መግቢያ ደጆች ማለትም ይሆናል። *ሕዝቤን በሐዘን እመታለሁ፤* ጕልማሳ በጦርነት ስለሚያልቅ፣ የይሁዳ ምድርና የኢየሩሳሌም ከተማ ልጆች አንዳቸው በሕይወት አይገኙም (ሕዝ5፥17 ይመ)። *አልተመለሱምና፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "ንስሓ አልገቡም" ማለት ሲሆን፣ በአሞ4፥6፡8-11 ላይ "ወደ እኔ አልተመለሳችሁም" ተብሎ የተጻፈውን ያስታውሳል፤ እዚያም ላይ ያለው የዕብራይስጥ ቃል ተመሳሳይ ነው (የ3፥1 ማብ ይመ)።

15፥8 *የመበለቶቻቸውን ቍጥር ከባሕር አሸዋ ይልቅ አበዛለሁ*፤ ዘርህን አበዛለሁ ተብሎ የተሰጠው የኪዳን ተስፋ (ዘፍ22፥17 እና ማብ ይመ) አሳዛኝ የሆነ የተገላቢጦሽ ሁኔታ ነው። *በቀትር … በድንገት*፤ በሞቃት አገር፣ ወታደራዊ ጥቃት ቀትር ላይ ቢሰነዘር የማይታሰብ ነውና አስደንጋጭ ይሆናል (የ6፥4 ማብ ይመ)። *አጥፊውን፤* ባቢሎንን ማለት ነው (የ4፥7 ማብ ይመ)። *ሽብርንና*፤ የ4፥19 ማብ ይመ።

15፥9 *የሰባቶቹ … ፤* ሙሉና በቂ ተብሎ የሚታመን የወንድ ልጆች ቍጥር ነው (ሩት4፥15 እና ማብ ይመ)፤ እነርሱ ወዲያው የሚጠፉ ነበሩ። *ገና ቀን ሳለ ፀሐይዋ ትጠልቃለች፤* አሞ8፥9 ይመ፤ ከማቴ27፥45 ጋር ያነጻጽሩ። *የተረፉትንም፤* "የቀሩትን" ማለት ነው (የ6፥9 ማብ ይመ)። እነርሱም ቢሆኑ ከሰይፍ አያመልጡም፤ ይገደላሉ (ሚክ6፥14 ይመ)።

*15፥10-21፤* ከኤርምያስ "ኑዛዜዎች" ይኸኛው ክፍል ሦስተኛው ነው፤ እዚህ ላይ እግዚአብሔር ለሁለቱ ኑዛዜዎች የሰጠው መልስ ይገኝበታል (ቍ11-14፡19-21)።

*15፥10፤* 20፥14-15፤ ኢዮ3፥3-10 ይመ። *እናቴ፤* ቍ8 ይመ። በብሉይ ኪዳን ላይ፣ ሁለት ተከታታይ የሆኑ አንቀጾች በዐበይት ቃላት ይተሳሰራሉ። *አላበደርሁም … አልተበደርሁም፤* ሰውን ከሰው ጋር ከሚያጋጭ ወይም ልብን ከሚከፋፍልና ሰውን

[11]*እግዚአብሔር* እንዲህ አለ፤
"በእርግጥ ለበጎ ዐላማ እታደግሃለሁ፤
በመከራና በጭንቅ ጊዜም፣
ጠላቶችህ ደጅ እንዲጠኑህ በእውነት
አደርጋለሁ።
[12]"ሰው ብረትን፣ ከሰሜን የመጣን ብረት፣
ነሐስንስ መስበር ይችላልን?
[13]በመላ አገርህ፣
ስላለው ኀጢአትህ ሁሉ፣
ሀብትና ንብረትህን፣
ያለ ዋጋ አሳልፌ ለምርኮ እሰጣለሁ።
[14]ቍጣዬ በላያችሁ፣
የሚነድ እሳት ትጭራለችና፣
በማታውቀው አገር፣
ለጠላቶችህ[a] ባሪያ አደርግሃለሁ።"

[15]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ ታውቃለህ፤
እንግዲህ አስበኝ፤ ጐብኘኝም፤
አሳዳጆቼን ተበቀልልኝ።
ታጋሽ እንደ መሆንህ አታጥፋኝ፤
ባንተ ምክንያት የሚደርስብኝን ነቀፋ
አስብ።
[16]ቃልህ በተገኘ ጊዜ በላሁት፤
የሠራዊት አምላክ *እግዚአብሔር* ሆይ፤
በስምህ ተጠርቻለሁና፣
ቃልህ ሐሤትና የልብ ደስታ ሆነልኝ።
[17]ፈንጠዝያ ከሚያደርጉት ጋር
አልተቀመጥሁም፤
ከእነርሱም ጋር አልፈነጠዝሁም፤
እጅህ በላዬ ስለ ነበር፣ በቍጣህ ስለ
ሞላኸኝ፣
ለብቻዬ ተቀመጥሁ።
[18]ሕመሜ ለምን ጸናብኝ?
ቍስሌስ ለምን በረታብኝ? ለምንስ
የማይፈወስ ሆነ?
እንደሚያታልል ወንዝ፣
እንደሚያሳስት ምንጭ ትሆንብኛለህን?
[19]ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"ብትመለስ፣ መልሼ አቆምሃለሁ፤
ታገለግለኛለህም፤
የከበረውን ከማይረባው ለይተህ ብትናገር፣
አፍ ትሆነኛለህ፤
እነርሱ ወደ አንተ ይመለሳሉ እንጂ፣
አንተ ወደ እነርሱ አትመለስም፤
[20]ለዚህ ሕዝብ የናስ ቅጥር፣ የተመሸገ የናስ
ቅጥር አደርግሃለሁ፤
ሊታደግህና፣ ላድንህም፣
እኔ ከአንተ ጋር ነኝና፤
ቢዋጉህም እንኳ፣
ሊያሸንፉህ አይችሉም፤"
ይላል *እግዚአብሔር*፤
[21]"ከክፉዎች እጅ እቤዥሃለሁ፤
ከጨካኞችም ጭምደዳ እታደግሃለሁ።"

**የጥፋት ቀን**

**16** የእግዚአብሔር ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ፤ [2]"በዚህ ስፍራ

15፥11 ቍ21፥ኤር 21፥1-2፤37፥3፤40፥4፤ 42፥1-3
15፥12 ዘጸ28፥48፤ ኤር28፥14፤ሰቆ1፥14፤ ሆሴ10፥11
15፥13 2ነገ25፥15፤ 24፥13፤መዝ44፥12፤ ኤር17፥3፤ሕዝ 38፥12-13
15፥14 ዘዳ28፥36፤ መዝ21፥9፤ኤር5፥19
15፥15 ዘፀ34፥6፤ መሳ16፥28፤መዝ 44፥22፤69፥7-9፤ 119፥84፤ኤር6፥10
15፥16 ኢዮ15፥11፤ መዝ119፥72፡103፤ ኢሳ43፥7፤ኤር14፥9 ፤ሕዝ2፥8፤3፥3፤ራእ 10፥10
15፥17 ሩት3፥3፤ 2ነገ3፥15፤መዝ1፥1፤ 26፥4-5፤ኤር16፥8
15፥18 ኢዮ6፥4፡15 ፤መዝ9፥10፤ኤር10፥ 19፤30፥12፤ሚክ1፥9
15፥19 ዘፀ4፥16፤ ዘካ3፥7
15፥20 መዝ129፥2 ፤ኢሳ50፥7፤ኤር1፥8፤ 20፥11፤42፥11፤ሕዝ 3፥8
15፥21 ዘፍ48፥16፤ መዝ97፥10፤ኤር1፥8 ፤50፥34
16፥2 ማቴ19፥12፤ 1ቆሮ7፥26-27

[a]14 አንዳንድ የዕብራይስጥ ጽሑፎች፣ ሰብዓ ሊቃናትና ሱርስት ጽሑፎች *ጠላቶችህ እንዲወስዱህ አደርጋለሁ* ይላሉ

ከሚለያይ ጉዳይ ውስጥ ገብቼ አላውቅም ማለት ነው።

*15፥11-14፤* በመጀመሪያ እግዚአብሔር ለኤርምያስ ይናገራል (ቍ11)፤ ከዚያም በኋላ ለይሁዳ ሕዝብ (ቍ12-14)።

*15፥11፤* እግዚአብሔር ኤርምያስን ያበረታታዋል። *ጠላቶችህ ደጅ እንዲጠኑህ በእውነት አደርጋለሁ፤* ለምሳሌ:- በ21፥1-2፤ 37፥3፤ 38፥14-26፤ 42፥1-3 ላይ ተፈጽሞአል።

*15፥12፤* አሉታዊ መልስ የማይሻ ጥያቄ ነው። *ብረት፤* የጥንካሬ ምልክት ነው (28፥13 ይመ)። *ከሰሜን፤* ከባቢሎን ምድር ማለት ነው (የኢሳ41፥25 ማብ ይመ)።

*15፥13-14፤* በ17፥3-4 ላይ በአብዛኛው ተደግሞ ይገኛል።

*15፥13፤* በ52፥17-23 ላይ ተፈጽሞአል። *ያለ ዋጋ፤* በኢሳ 55፥1 ጋር ያነጻጽሩ። ሰውም ሆነ የምርኮ ንብረት በቀላሉ በነጻ የሚወሰዱ ይሆናሉ (የኢሳ52፥3 ማብ ይመ)።

15፥14 *ቍጣዬ … እሳት ትጭራለችና፤* ከዘዳ32፥22 ቃል በቃል የተወሰደ ሐሳብ ነው።

15፥15 *አንተ ታውቃለህ፤* ኤርምያስ ያለፈበትን መከራ እግዚአብሔር ያውቃል (ቍ10 ይመ)። *አስበኝ፤* የእኔ ነገር እንደሚገድህ ግለጽ ማለት ነው(የዘፍ8፥1 ማብ ይመ)።

15፥16 *ቃልህ … በላሁት፤* ቃልህን አሰላስላለሁ፤ ከራሴ ጋር አዋሕድሁት፤ አካሌም አደረግሁት ማለት ነው (ሕዝ2፥8-3፥3፤ ራእ10፥9-10 ይመ)። *በተገኘ ጊዜ፤* "በመጣ ጊዜ" ማለትም ይቻላል፤ የሚያመለክተውም የሕጉ መጽሐፍ በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት በ621 ዓ.ቅ.ክ በቤተ መቅደስ ውስጥ መገኘቱን ሳይሆን አይቀርም (2ነገ22፥13፤ 23፥2 ይመ፤ በተጨማሪም የ1፥2 ማብ ይመ)። *በስምህ ተጠርቻለሁና፤* 14፥9 ይመ፤ የአንተው ነኝ ማለት ነው (የ7፥10 ማብ ይመ)። … *ሐሤትና የልብ ደስታ ሆነልኝ፤* መዝ1፥2 ይመ።

15፥17 *ለብቻዬ ተቀመጥሁ፤* ኤርምያስ ሚስት አግብቶና በትዳር ተጠምዶ አያውቅም (16፥1 ይመ)፤ የቅርብ ጓደኞቹም እጅግ ጥቂት ነበሩ። *እጅህ፤* የእግዚአብሔርን ተግሣጽ የሚያመለክት ነው (2ነገ3፥15፤ ኢሳ8፥11 እና ማብ፤ ሕዝ1፥3፤ 3፥14፡22፤ 37፥1፤ 40፥1 ይመ)። *በቍጣህ፤* ኤርምያስ በቍጣ የተሞላው ከይሁዳ በደል የተነሣ ነበር (6፥11 ይመ)።

*15፥18፤* ኤርምያስ በውስጡ ይሰማው የነበረውን፣ ስለ ተለእኮውና ስለ እግዚአብሔር ታማኝነት ማመንታቱን መልስ በማይሹ በሁለት ጥያቄዎች ይገልጣል። *ሕመሜ … ጸናብኝ? ቍስሌስ … በረታብኝ?* ኢየሩሳሌምም በ30፥12-15 በዚሁ መልክ ተገልጻለች፤ ከዚህም ጋር የእግዚአብሔር ፈዋሽነት ተያይዞ ተጠቅሶአል (30፥17)። *ትሆንብኛለህን?* መዝ22፥1፤ ማቴ27፥46 ይመ። *እንደሚያታልል ወንዝ* "ማታለል" የሚለው ቃል በኢዮ6፥15-20 ላይ ዐልፎ ዐልፎ ውሃ የሚገኝባቸውን ጅረቶች ይገልጣል (በሚክ1፥14 ይመ)። እዚህ ላይ ኤርምያስ እግዚአብሔር ቀደም ሲል፣ "እኔ የሕያው ውሃ ምንጭ ነኝ" ብሎት ስለ ነበር (2፥13 እና ማብ ይመ)፣ ካለበት ሁኔታ ጋር በማመዛዘን ለእግዚአብሔር ቅሬታውን ያሰማል።

*15፥19-21፤* እግዚአብሔር በዚህ ክፍል ላይ ኤርምያስ ንስሐ እንዲገባ ያዘዋል፤ ከዚያም እያበረታታው የተልእኮውን ጥሪ ያድስለታል።

15፥19 *ብትመለስ መልሼ አቆምሃለሁ … ይመለሳሉ እንጂ … አትመለስም፤* ለእነዚህ አራት ቃሎችና ሐረጎች የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል፣ ለአራቱም ከአንድ ሥርወ ቃል የመጣ ነው (የ3፥1 ማብ፤ ኢሳ1፥25-26 ይመ)። *ታገለግለኛለህም፤* የዕብራይስጡ ቃል በቁሙ ሲተረጐም፣ "በፊቴ ትቆማለህ" የሚል ነው፤ ይህም የታዛዥ አገልጋይን ተገቢ አቀራረብ ያመለክታል (ዘኍ16፥9፤ ዘዳ10፥8 ይመ)። አፍ ትሆነኛለህ፤ "ስለ እኔ ሆነህ ትናገርልኛለህ" ማለት ነው (1፥9 እና ማብ፤ ዘፀ4፥15-16 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፀ7፥1-2 ማብ ይመ)።

*15፥20፤* 1፥8፡18-19 እና ማብ ይመ።

15፥21 *ከክፉዎች … እቤዥሃለሁ፤* ለምሳሌ:- 36፥26፤ 38፥6-13 ይመ።

*16፥1-17፥18፤* በዚህ ክፍል ውስጥ የመከራና የማጽናናት ቃል ይገኝበታል፤ ሆኖም ስለ መከራ የተነገረው ይበዛል (16፥1-13፡16-18፤ 16፥21-17፥6፤ 17፥9-13፡18)። የመጀመሪያው ግማሽ ክፍል በስድ ንባብ የቀረበ ሲሆን (16፥1-18)፣ የቀረው ግማሽ ክፍል ደግሞ በግጥም መልክ የቀረበ ነው (16፥19-17፥18)።

*16፥2፤* ኤርምያስ የቤት ሰብ ማበረታቻና ድጋፍ ሳያገኝ፣

ሚስት አታግባ፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆችም አይኑሩህ፤” [3]በዚህች ምድር ስለሚወለዱ ወንዶችና ሴቶች ልጆች፣ እንዲሁም ስለ እናቶቻቸው ስለ አባቶቻቸው *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ [4]“በአደገኛ በሽታ ይሞታሉ፤ አይለቀስላቸውም፤ አይቀበሩም፤ በምድርም ላይ እንደ ጕድፍ ይጣላሉ:: በሰይፍና በራብ ይጠፋሉ፤ሬሳቸውም ለሰማይ ወፎችና ለምድር አራዊት መብል ይሆናል::”

[5]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ “በረከቴን፣ ፍቅሬንና ምሕረቴን ከዚህ ሕዝብ አርቄ አለሁና፤ ልቅሶ ወዳለበት ቤት አትግባ፤ ታለቅስና ታዝንም ዘንድ አትሂድ” ይላል *እግዚአብሔር*:: [6]“ታላላቆችና ታናናሾች በዚህች ምድር ይሞታሉ፤ አይቀበሩም፤ አይለቀስላቸውም፤ ሰውነቱን የሚቧጥጥላቸው፣ ጠጕሩንም የሚላጭላቸው አይገኝም፤ [7]ሐዘንተኞችን ለማጽናናት የእዝን እንጀራ የሚያመጣ አይኖርም፤ አባትም ሆነ እናት የሞተባቸውንም ለማጽናናት መጠጥ የሚያቀርብ አይገኝም::

[8]“ከእነርሱ ጋር ተቀምጠህ ለመብላትና ለመጠጣት ድግስ ወዳለበት ቤት አትግባ፤ [9]የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ ‘እነሆ፤ በዐይናችሁ ፊት፣ በዘመናችሁም የደስታና የሐሤት ድምፅ፣ የሙሽራውንና የሙሽራዪቱን ድምፅ ከዚህ ስፍራ አስወግዳለሁ::’

[10]“ይህን ሁሉ ለዚህ ሕዝብ በምትነግርበት ጊዜ ሰዎቹ፣ ‘*እግዚአብሔር* ይህን ሁሉ ታላቅ ጥፋት በእኛ ላይ ለምን ዐወጀ? በደላችንስ ምንድን ነው? በአምላካችን *በእግዚአብሔር* ላይ የሠራነው ኀጢአት ምንድን ነው?’ ብለው ቢጠይቁህ፣ [11]እንዲህ ትላቸዋለህ፤ ‘አባቶቻችሁ እኔን ስለተውኝ ነው’ ይላል *እግዚአብሔር*፤ ‘ሌሎችን አማልክት በመከተል፣ ስላገለገሏቸውና ስላመለኳቸው ነው፤ ትተውኝ ኰበለሉ፤ ሕጌንም አልጠበቁም:: [12]እናንተም ደግሞ ከአባቶቻችሁ የባሰ ክፉ ነገር አድርጋችኋል፤ እያንዳንዳችሁ እኔን በመታዘዝ ፈንታ የልባችሁን ክፋት ምን ያህል በእልኸኝነት እንደምትከተሉ ተመልከቱ:: [13]ስለዚህ ከዚህች ምድር አውጥቼ፣ እናንተም ሆነ አባቶቻችሁ ወደ ማታውቁት ምድር እጥላችኋለሁ፤ ምሕረትንም አላደርግላችሁምና በዚያ ሌሎችን አማልክት ቀንና ሌሊት ታገለግላላችሁ::’

[14]“ስለዚህ ሰዎች:- ‘እስራኤላውያንን ከግብፅ ምድር ያወጣ ሕያው *እግዚአብሔርን*’ ብለው ከእንግዲህ የማይምሉበት ዘመን ይመጣል” ይላል *እግዚአብሔር*፤ [15]“ነገር ግን፣ ‘እስራኤላውያንን ከሰሜን ምድርና እነርሱን ከበተነባቸው ከሌሎች አገሮች ሁሉ ያወጣ ሕያው *እግዚአብሔርን*’ ይላሉ፤ ለአባቶቻቸው ወደ ሰጠኋቸው ምድር እመልሳቸዋለሁና::

[16]“አሁን ግን ብዙ ዓሣ አጥማጆችን እልካለሁ” ይላል *እግዚአብሔር*፤ “እነርሱም ያጠምዷቸዋል:: ከዚያም በኋላ ብዙ አዳኞችን እሰዳለሁ፤ እነርሱም ከየተራራው፣ ከየኰረብታው ሁሉ ከየዐለቱም ስንጣቂ አድ

16፥3 ኤር6፥21
16፥4 ቍ6፤ዘዳ28፥26፤መዝ79፥1-3፤ኤር9፥22፤14፥12:15፤19፥7፤25፥33
16፥5 ኤር15፥5
16፥6 ቍ4፤ዘሌ19፥28፤21፥5፤ኢዮ1፥20፤ኤር9፥21፤ሕዝ9፥5-6
16፥7 2ሳሙ3፥35፤ኤር22፥10፤ሰቆ1፥9:11፤ሕዝ24፥17፤ሆሴ9፥4
16፥8 ዘፀ32፥6፤መክ7፥2-4፤ኤር15፥17
16፥9 መዝ78፥63፤ኢሳ22፥12-14፤24፥8፤51፥3፤ሕዝ 26፥13፤አሞ 6፥4-7፤ራእ18፥23
16፥10 ዘዳ29፥24፤ኤር5፥19
16፥11 ዘዳ29፥25-26፤1ነገ9፥9፤ኢዮ31፥27፤መዝ106፥35-43
16፥12 ዘፀ32፥8፤መክ9፥3፤ኤር3፥17፤7፥26፤ሕዝ20፥30፤አሞ2፥4፤
16፥13 ዘዳ4፥28፤28፥36፤1ነገ9፥9፤2ዜና7፥20፤ኤር5፥19፤15፥5
16፥14 ዘዳ15፥15፤ኤር29፥10፤30፥3፤31፥27:38
16፥15 ዘዳ30፥3፤መዝ53፥6፤ኢሳ11፥11:12፤14፥1፤ኤር3፥18፤23፥8፤30፥3፤32፥44፤ሕዝ38፥14፤ኢል3፥1

---

አገልግሎቱንና የሕይወቱን ውጣ ውረድ ብቻውን ተወጣው (የ15፥17 ማብ ይመ):: *አታግባ ... አይኑሩህ፤* በዕብራይስጥ ይህ ሐረግ ጥብቅ ትእዛዝ ያስተላልፋል፤ ትእዛዙ ጠንከር ያለ አሉታዊ ትእዛዝ ነው፤ ይኸውም በዐሠርቱ ትእዛዛት ውስጥ እንዳለው ዐይነት ነው (ዘፀ20፥3-4:7:13-17 ይመ):: *በዚህ ስፍራ፤* በይሁዳና በኢየሩሳሌም ማለት ሲሆን፣ በተለይ ኢየሩሳሌምን የሚያመለክት ነው (ለምሳሌ:- ሶፎ1፥4 ይመ)::

16፥4 *በሽታ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በ14፥18 ላይ “የወደቁትን” ተብሉ ተተርጕሞአል:: *አይለቀስላቸውም፤ አይቀበሩም፤* ቍ6፤ 7፥33 እና ማብ፤ 8፥2፤ 14፥16፤ 25፥33 ይመ:: *ጕድፍ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም በዕብራይስጡ፣ “ፍግ” ማለት ነው (8፥2፤ 9፥22፤ 25፥33 ይመ):: *በሰይፍና በራብ ይጠፋሉ፤* 14፥15-16 ይመ፤ በተጨማሪም የ5፥12 ማብ ይመ:: *ለሰማይ ወፎችና ለምድር አራዊት መብል፤* የ7፥33 ማብ ይመ::

16፥5 *ልቅሶ ወዳለበት ... አትግባ፤* እግዚአብሔር የሰጠውን ተመሳሳይ ትእዛዝ በሕዝ24፥16-17:22-23 ላይ ይመ::

16፥6 *ሰውነቱን የሚቧጥጥላቸው፣ ጠጕሩን የሚላጭላቸው፤* እንደዚህ ዐይነቱ የሐዘን መግለጫ በአሪት ሕግ የተከለከለ ነበር (ዘሌ19፥28፤ 21፥5 እና ማብ፤ ዘዳ14፥1 እና ማብ ይመ)፤ ሆኖም እስራኤላውያን ዐልፎ ዐልፎ ይፈጽሙት ነበር (41፥5፤ ሕዝ7፥18፤ ሚክ1፥16 ይመ)::

*16፥7፤* የእዝን እንጀራ ለቀስተኞች ቤት መውሰድ በእስራኤልም ባህል የተለመደ ነው (2ሳሙ3፥35፤ 12፥16-17፤ ሕዝ24፥17:22፤ ሆሴ9፥4 ይመ):: *ለማጽናናት መጠጥ፤* ይህ ሐረግ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “የመጽናኛ” የሚል አገባብ አለው፤ በኋለኛው ዘመን በነበረው የአይሁድ ሃይማኖታዊ ሥርዐት መሠረት ለዋነኛው ባለ ሐዘን ጠጅ ተሞልቶ የሚሰጠው በልዩ ጽዋ ነበር::

16፥8 *ወዳለበት ቤት አትግባ፤* ዘመኑ ደግሶ ለመፈንጠዝም ሆነ ተቀምጦ ከሐዘን ለማጽናናት አመቺ ጊዜ አልነበረም (ቍ5 ይመ)::

*16፥9፤* 7፥34፤ 25፥10 ይመ፤ ከ33፥10-11 ጋር ያገናዝቡ::

*16፥10-13፤* በ5፥19 ላይ ከተነሣው ጥያቄ ጋር አንድ ዐይነት ነው፤ ሆኖም በዚህኛው ክፍል የተሰጠው መልስ ሰፋ ያለ ነው (9፥12-16፤ 22፥8-9፤ ዘዳ29፥24-28፤ 1ነገ9፥8-9 ይመ)::

*16፥10፤* በሚል 1፥6-7፤ 2፥17፤ 3፥7-8:13 ላይ ከቀረቡት ተመሳሳይ ጥያቄዎች ጋር ያነጻጽሩ::

*16፥11፤* በዚህ ክፍል የተጠቀሱት ሰዎች የሠሩትን ኀጢአት መፈጸም ከእግዚአብሔር ጋር የገቡትን ኪዳን ማፍረስ እንደ ሆነ የተገለጠበትን፣ 11፥10 ይመ::

16፥12 *ከአባቶቻችሁ የባሰ ክፉ ነገር አድርጋችኋል፤* 1ነገ14፥9 ይመ:: ሊመጣባቸው ያለው ፍርድና ቅጣት ከእነርሱ በፊት ከነበሩት ትውልዶች ኀጢአት የተነሣ ነው ብሎ ማሰብና ምክንያት መስጠት አይቻልም (31፥29-30፤ ሕዝ18፥2-4 ይመ):: *የልባችሁን ክፋት ... በእልኸኝነት እንደምትከተሉ፤* የ3፥17 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 7፥24 ይመ::

*16፥13፤* ዘዳ28፥36:64 ይመ:: *አውጥቼ ... እጥላችኋለሁ፤* ወደ ምርኮ ማለት ነው (7፥15፤ 22፥26፤ ዘዳ29፥28 ይመ):: *እናንተም ሆነ አባቶቻችሁ ወደማታውቁት ምድር፤* የባቢሎን ምድር ነው (9፥16 ይመ)::

*16፥14-15፤* ቃሉ በአብዛኛው በ23፥7-8 ላይ ካለው ጋር አንድ ዐይነት ነው:: ክፍሉ የእስራኤልን ሕዝብ የአንድ ሺህ ዓመት ታሪክ ቢጋር ማለትም ከግብፅ ባርነት ነጻ የወጡበትን (1446 ዓ.ቅ.ክ ገደማ)፣ የምርኮውን ዘመን (586 ዓ.ቅ.ክ)፣ ከምርኮ የተመለሱበትን ጊዜ (538 ዓ.ቅ.ክ.) ይገልጣል:: ኢሳ43፥16-21፤ 48፥20-21፤ 51፥9-11 ይመ:: *ሕያው እግዚአብሔርን፤* የዘፍ42፥15 ማብ ይመ::

16፥15 *ከሰሜን ምድርና፤* የባቢሎንን ምድር የሚያመለክት ነው (የኢሳ41፥25 ማብ ይመ)::

16፥16 *ዓሣ አጥማጆችን ... አዳኞችን፤* ድል አድራጊ ወገኖችን ያመለክታል (ሕዝ12፥13፤ 29፥4፤ አሞ4፥2 እና ማብ ይመ):: *ከየተራራው ከየኰረብታው፤* ሕዝቡ ከጠላቱ አምልጦ ላያመልጥ የሚሸሸግባቸው ናቸው (4፥29 እና ማብ ይመ):: *ከየዐለቱም ስንጣቂ፤* ይህ አባባል ከኤርምያስ መጽሐፍ ውጭ ተጠቅሶ የሚገኘው በኢሳ7፥19 ላይ ብቻ ነው:: እግዚአብሔር እዚህ ላይ

ነው ይደዟቸዋል:: [17]ዐይኔ በመንገዳቸው ሁሉ ላይ ነው፤ በፊቴ የተገለጡ ናቸው፤ ኀጢአታቸውም ከዐይኔ የተሰወረ አይደለም:: [18]ምድሬን በድን በሆኑ አስጸያፊ ጣዖቶቻቸው ስላረከሱ፣ ርስቴንም በአሳፋሪ ነገሮች ስለሞሉ፣ ላደረጉት በደልና ኀጢአት ዕጥፍ እከፍላቸዋለሁ::"

[19]ብርታቴና ምሽጌ፣
በመከራ ቀን መጠጊያዬ የሆንህ
*እግዚአብሔር* ሆይ፤
አሕዛብ ከምድር ዳርቻ፣
ወደ አንተ መጥተው እንዲህ ይላሉ፤
"አባቶቻችን ለአንዳች ነገር ያልረቧቸውን
ከንቱ ጣዖቶች፣
የሐሰት አማልክትን ወረሱ::
[20]ሰዎች ለራሳቸው አማልክትን ያበጃሉን?
ያደርጉ ይሆናል፤ እንዲህ ዐይነቶቹ ግን
አማልክት አይደሉም::"
[21]"ስለዚህ አስተምራቸዋለሁ፤
ኀይሌንና ታላቅነቴን፣
አሁን አስተምራቸዋለሁ፤
እነርሱም ስሜ *እግዚአብሔር*፣
እንደ ሆነ ያውቃሉ::

**17** "የይሁዳ ኀጢአት በብረት ብርዕ፣
በሾለ የአልማዝ ጫፍ፣ ተጽፎአል፤
በልባቸው ጽላት፣
በመሠዊያቸውም ቀንዶች ላይ
ተቀርጾአል::
[2]ልጆቻቸው እንኳ ሳይቀሩ፣
በለመለሙ ዛፎች ሥር፣
ከፍ ባሉ ኰረብቶችም ላይ ያሉትን፣
መሠዊያቸውንና አሼራ የተባለችውን
ጣዖት ምስል[x] ያስባሉ::
[3]በአገርህ ሁሉ ከተፈጸመው ኀጢአት
የተነሣ፣
በምድሪቱ ያለህ ተራራዬ፣[y]
ሀብትህንና ንብረትህን ሁሉ፣
መስገጃ ኰረብቶችህንም ጭምር፣
ለብዝበዛ አደርገዋለሁ::
[4]በገዛ ጥፋትህ፣
የሰጠሁህን ርስት ታጣለህ፤
በማታውቀውም ምድር፣
ለጠላቶችህ ባሪያ አደርግሃለሁ፤
ለዘላለም የሚነደውን፣
የቍጣዬን እሳት ጭረሃልና::"
[5]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"በሰው የሚታመን፣
በሥጋ ለባሽ የሚመካ፣
ልቡንም *ከእግዚአብሔር* የሚያርቅ
የተረገመ ነው::
[6]በምድረ በዳ እንዳለ ቍጥቋጦ ይሆናል፤

[x]2 ወይም *የአሼራ ዐጸድ*
[y]3 ወይም *በምድሪቱ ያሉ ተራራዎቼን*

16፥16 1ሳሙ26፥20፤አሞ4፥2፤9፥3፤ሚክ7፥2፤ዕን1፥14-15
16፥17 ዘፍ3፥8፤ ምሳ15፥3፤መክ12፥14፤መዝ51፥9፤ሰፎ1፥12፤ማር4፥22፤1ቆሮ4፥5፤ዕብ4፥13
16፥18 ዘኍ35፥34፤1ነገ14፥24፤መዝ101፥3፤ኢሳ65፥6፤40፥2፤2፥7፤4፥1፤12፥3፤ሕዝ5፥11፤8፥10፤ራእ18፥6
16፥19 ዘጸ32፥21፤1ሳሙ12፥21፤2ሳሙ22፥3፤መዝ4፥2፤46፥1፤ኢሳ2፥2፤40፥19፤ኤር3፥17፤14፥22
16፥20 መዝ115፥4-7፤ኤር2፥11፤ሮሜ1፥23
16፥21 ዘፀ 3፥15
17፥1 ዘፀ 27፥2፤ ዘዳ6፥6፤ኢዮ19፥24፤2ቆሮ3፥3
17፥2 2ዜና24፥18፤ኤር2፥20
17፥3 2ነገ24፥13፤ኤር26፥18፤15፥13፤ሚክ3፥12
17፥4 ዘዳ28፥48፤ኤር7፥20፤12፥7፤16፥13፤22፥28፤ሰቆ5፥2
17፥5 መዝ108፥12፤ኢሳ2፥22፤2ቆሮ1፥9
17፥6 ዘዳ29፥23፤ኢዮ30፥3፤39፥6፤መዝ107፥34፤ኤር48፥9

ምናልባት "በዐለት ስንጣቂ" ውስጥ እንዳለች በስብሳ የተበላሸችውን ከተልባ እግር የተሠራችውን በፍታ ጨርቅ ሊያሳስብ የተናገረው ይሆናል (13፥4)::

16፥17 *ዐይኔ በመንገዳቸው ሁሉ ላይ ነው፤* 32፥19 ይመ:: *ከዐይኔ የተሰወረ አይደለም፤* 23፥24 ይመ::

16፥18 *ዕጥፍ እከፍላቸዋለሁ፤* 17፥18፤ ኢሳ40፥2 እና ማብ ይመ:: *ምድሬን ... ስላረከሱ፤* በነበራቸው የመንጻት ሕግ መሠረት ራሳቸውን ጠብቀው ባለመገኘታቸው አረከሱት (2፥7፤ 3፥1-2 ይመ፤ በተጨማሪም የዘሌ4፥12 ማብ ይመ):: *በድን በሆኑ አስጸያፊ ጣዖቶቻቸው፤* ዘሌ26፥30 ይመ፤ ጣዖታት የራሳቸው የሆነ ሕይወት የላቸውም (መዝ115፥4-7፤ 135፥15-17 ይመ):: *ርስቴንም፤* የእግዚአብሔር ምድር (17፥4 ይመ፤ በተጨማሪም የ2፥7 ማብ ይመ):: *በአሳፋሪ፤* በእግዚአብሔር ፊት አስጸያፊና አስነዋሪ በሆኑ ሁሉ ማለት ነው (2፥7 ይመ፤ በተጨማሪ የዘሌ 7፥21 ማብ ይመ)::

*16፥19-20፤* ነቢዩ በዚህ ክፍል ጥቂት አጫጭር የተስፋ ቃላትን ጠቄም ጠቄም ያደርጋል::

16፥19 *ብርታቴና ... ምሽጌ፣ ... በመከራ ቀን መጠጊያዬ፤* እግዚአብሔር መመኪያና የሚጠብቅ ኀያል አምላክ መሆኑን የሚያመለክቱ ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆኑ አባባሎች በዳዊት መዝሙር የተለመዱ ናቸው (ለምሳሌ ያህል:- መዝ18፥1-2፤ 28፥7-8፤ 59፥9: 16-17 ይመ):: *አሕዛብ ... ወደ አንተ መጥተው ...፤* 4፥2 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ2፥2-4፤ 42፥4፤ 45፥14፤ 49፥6፤ ዘካ8፥20-23፤ 14፥16 ይመ:: *ከንቱ ጣዖቶች፤* 2፥5 ማብ ይመ:: *ለአንዳች ... ያልረቧቸውን፤* ያስገኙላቸው ጥቅም አልነበረም (የ2፥8 ማብ ይመ):: *የሐሰት አማልክት፤* 5፥7 ይመ::

*16፥21-17፥4፤* በቍ1 ላይ እግዚአብሔር ለኤርምያስ በመልስነት የጀመረውን ብርቱ ማስጠንቀቂያ በዚህም ላይ ይቀጥላል::

16፥21 *አስተምራቸዋለሁ ... አስተምራቸዋለሁ ... ያውቃሉ፤* በዕብራይስጡም የሦስቱ ቃላት መሠረት አንድ ነው:: እግዚአብሔር "እንዲያውቁ ያደርጋቸዋል"፤ እነርሱም በእርግጥ "ያውቃሉ":: አስተምራቸዋለሁ፤ እነርሱም ያውቃሉ ቢል የይሁዳን ሕዝብና ሌሎቹንም ሕዝቦች ጭምር ማለቱ ሊሆን ይችላል (ሕዝ36፥23፤ 37፥14 ይመ):: *ስሜ እግዚአብሔር እንደ ሆነ ያውቃሉ፤* በብሉይ ኪዳን "ስም" ሲባል ብዙ ጊዜ "ማንነትን" ወይም "እርሱ ማን እንደ ሆነ" ማለት ነው (የመዝ5፥11 ማብ ይመ):: ኤርምያስ "ስሜን ያውቃሉ" ለሚለው፣ ሕዝቅኤል፣ "እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ" የሚል አቻ የሆነ አገላለጽ አለው::

17፥1 *የይሁዳ ኀጢአት፤* ባዕድ አምልኮ ማለት ነው፤ ለእግዚአብሔር ታማኝ ባለመሆናቸውና ጣዖትን በመከተላቸው አገር አልባ ሆነው በባርነት እንደሚጋዙ ተወስኖባቸዋል (ቍ4ይመ):: *በብረት ብርዕ ... ተጽፎአል፤* ለዘለቄታ እንዲቈዩ የሚፈለጉ የቀረጻ ጽሑፎች የሚጻፉበት ዘዴ ይህ ነበር (ኢዮ 19፥24 ይመ):: *አልማዝ፤* እጅግ ጠንካራ የሆነ የጥንት ሰዎች ይጠቀሙበት የነበረ ክቡር ድንጋይ ነው (ሕዝ3፥9፤ ዘካ7፥12 ይመ):: *በልባቸው ጽላት፤* በተመሳሳይ የአነጋገር ዘይቤ ሰፍሮ የሚገኘውን ምሳ3፥3፤ 7፥3 ይመ:: *በመሠዊያቸውም ቀንዶች፤* የይሁዳ ሕዝብ ከእግዚአብሔር እጅግ የራቀ ስለ ነበር ኀጢአታቸው ተቀርጾ የሚገኘው በልባቸው ላይ ብቻ ሳይሆን፣ በመሠዊያቸውም ላይ ነበሩ፤ ይህም ለስርየት ሳይሆን በእግዚአብሔር ዘንድ ታስቦ እንዲቈይ ነበር (ዘሌ16፥18 ይመ)::

17፥2 *በለመለሙ ዛፎች ... ከፍ ባሉ ኰረብቶችም፤* የ2፥20 ማብ ይመ:: *መሠዊያቸውንና አሼራ የተባለችውን ጣዖት ምስል፤* የዘፀ34፥13፤ የዘዳ7፥5 ማብ ይመ::

*17፥3-4፤* ከሞላ ጐደል በ15፥13-14 ላይ ካለው ጋር ይቀራረባል (የዚያኑ ክፍል ማብ ይመ)::

17፥3 *ተራራዬን፤* በኢየሩሳሌም ውስጥ ቤተ መቅደሱ የነበረበትን የጽዮን ተራራ የሚያመለክት ነው (መዝ24፥3፤ ኢሳ 2፥3፤ ዘካ8፥3 ይመ):: *መስገጃ ኰረብቶች፤* ባዕድ አምልኮ የሚካሄድባቸው ቦታዎች ነበሩ::

17፥4 *ርስት፤* የከነዓን ምድር ነው (16፥18 ይመ፤ በተጨማሪም የ2፥7 ማብ ይመ)::

*17፥5-8፤* መዝ1 እና ማብ ይመ::

17፥5 *የተረገመ፤* የ11፥3 ማብ ይመ:: *ሥጋ፤* የ"መንፈስ" ተቃራኒ ነው (ኢሳ31፥3 ይመ፤ በተጨማሪም ኢዩ10፥4 ይመ)::

17፥6 *ቍጥቋጦ፤* 48፥6 ይመ፤ ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል ከእነዚህ ሁለት ቦታዎች ውጭ የሚገኘው ቦታ በመዝ

መልካም ነገር ሲመጣ አያይም፤
ሰው በሌለበት በጨው ምድር፣
በምድረ በዳ በደረቅ ስፍራ ይቀመጣል።

[7]“ነገር ግን በእግዚአብሔር የሚታመን፣
መታመኛውም እግዚአብሔር የሆነ ሰው
ቡሩክ ነው።
[8]በውሃ ዳር እንደ ተተከለ፣
ሥሩንም ወደ ወንዝ እንደሰደደ
ዛፍ ነው፣
ሙቀት ሲመጣ አይፈራም፤
ቅጠሉም ዘወትር እንደለመለመ ነው፤
በድርቅ ዘመን አይሠጋም፤
ፍሬ ማፍራቱንም አያቋርጥም።”

[9]የሰው ልብ ከሁሉ ይልቅ ተንኰለኛ ነው፤
ፈውስም የለውም፤
ማንስ ሊረዳው ይችላል?

[10]“እኔ እግዚአብሔር ለሰው ሁሉ እንደ
መንገዱ፣
እንደ ሥራው ፍሬ ለመስጠት፣
ልብን እመረምራለሁ፤
የአእምሮንም ሐሳብ እፈትናለሁ።”

[11]ሀብትን በግፍ የሚያከማች ሰው፣
ያልፈለፈለችውን ጫጩት
እንደምትታቀፍ ቆቅ ነው፤
በዕድሜው አጋማሽ ትቶት ይሄዳል፤
በመጨረሻም ሞኝነቱ ይረጋገጣል።

17፥7 መዝ146፥5፤ 26፥1፤34፥8፤40፥4፤ምሳ16፥20፤ኤር39፥18
17፥8 ኢዮ14፥9፤ መዝ1፥3፤92፥12-14፤ ኤር14፥1-6፤ሕዝ 19፥10፤47፥12
17፥9 መክ9፥3፤ ማቴ13፥15፤ማር 7፥21-22
17፥10 ዘሌ26፥28፤ ኢሱ22፥22፤2ዜና 6፥30፤መዝ17፥3፤ 62፥12፤139፥23፤ኤር 11፥20፤12፥13፤14፥1 6፤20፥12፤21፥14፤ 32፥19፤ሕዝ11፥5፤ 38፥10፤ማቴ16፥27፤ ራእ2፥23
17፥11 ሉቃ12፥20
17፥12 ኤር 3፥17
17፥13 መዝ69፥28 ፤71፥5፤87፥6፤ኢሳ 12፥3፤ኤር2፥17፤ 14፥8፤ሕዝ13፥9፤ዳን 12፥1፤ዮሐ4፥10
17፥14 ዘፀ15፥21፤ ኢሳ30፥26፤መዝ 109፥1፤ 119፥94፤ ኤር15፥18
17፥15 ኢሳ5፥19፤ 2ጴጥ3፥4
17፥16 መዝ139፥4
17፥17 መዝ18፥18 ፤46፥1፤88፥15-16፤ ኤር16፥19፤ናሆ1፥7
17፥18 መዝ35፥1-8 ፤ኢሳ40፥2፤ኤር12፥3

[12]የመቅደሳችን ስፍራ፣
ከጥንት ጀምሮ ከፍ ያለ የክብር ዙፋን
ነው።
[13]የእስራኤል ተስፋ እግዚአብሔር ሆይ፤
ጥለውህ የሚሄዱ ሁሉ ያፍራሉ፤
ፊታቸውን ከአንተ የሚመልሱ በዐፈር ላይ
ይደፋሉ፤
የሕይወትን ውሃ ምንጭ፣
እግዚአብሔርን ትተዋልና።

[14]እግዚአብሔር ሆይ፤ ፈውሰኝ፤ እፈወሳለሁ፤
አድነኝ እኔም እድናለሁ፤
አንተ ምስጋናዬ ነህና።
[15]እነርሱ ደጋግመው፣
“የእግዚአብሔር ቃል የት አለ?
እስቲ አሁን ይፈጸም!” ይሉኛል።
[16]እረኛ ሆኜ አንተን ከማገልገል ወደ
ኋላ አላልሁም፤
ክፉ ቀን እንዲመጣ አልተመኘሁም ታውቃለህ፤
ከአንደበቴ የሚወጣውም በፊትህ
ግልጽ ነው።
[17]አስደንጋጭ አትሁንብኝ፤
በመከራ ቀን መሸሸጊያዬ አንተ ነህ።
[18]አሳዳጆቼ ይፈሩ፤
እኔን ግን ከዕፍረት ጠብቀኝ፤
እነርሱ ይደንግጡ፤
እኔን ግን ከድንጋጤ ሰውረኝ፤
ክፉ ቀን አምጣባቸው፤
በዕጥፍ ድርብ ጥፋት አጥፋቸው።

---

102፥17 ላይ ብቻ ነው፤ በዚያም “የተራቈተ” የሚል ይሰጣል።

17፥7 *የሚታመን፣ መታመኛውም፤* ልክ እንደ አማርኛው የእነዚህ ሁለት ቃላት ሥርወ ቃል ተመሳሳይ ነው።

17፥8 *ተተከለ፤* “ከሌላ ቦታ መጥቶ የተተከለ” ማለት ይቻላል። *ውሃ፤* የጻድቅ ሰው የብርታት ምንጭ ተብሎ የተጠቀሰውን ተመሳሳይ የዕብራይስጥ ሥርወ ቃል በኢሳ44፥4 ይመ። *በድርቅ፤* የ14፥1 ማብ ይመ። *ፍሬ ማፍራቱንም …፤* ኤርምያስ በ12፥1-2 ላይ ላቀረበው አቤቱታ እግዚአብሔር የሰጠው መልስ ነው (የዚያንኑ ማብ ይመ)።

*17፥9፤* ነቢዩ በመጀመሪያ ሁኔታውን በማስተዋል ይመለከታል፤ ከዚያም በኋላ መልስ የማይሻ ጥያቄ ይጠይቃል። ይህም ሰው በተፈጥሮ ምን ያህል ክፉ እንደ ሆነ የሚያመለክት ነው። *ልብ፤* “የሕይወት መመንጫ” የሆነው የሰው ልብ ክፋት በውስጡ ባይበቅል መልካም ነበር (ምሳ4፥23)። *ተንኰለኛ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ሥርወ ቃል “ያዕቆብ” ለሚለውም ስም መሠረት ነው (ያዕቆብ ማለት “ተረከዝ ጉታች” ማለት ሲሆን፣ የዘይቤያዊ አባባሉ ትርጒም፣ “አታላይ” ማለት ነው)።

*17፥10፤* እዚህ ላይ እግዚአብሔር ለኤርምያስ ጥያቄ መልስ እየሰጠ ነው። *እንደ መንገዱ፤* ይህ ሐረግ ከዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “የሥራውን ፍሬ” የሚል ይሆናል (ከ6፥19 ጋር ያነጻጽሩ)። *እመረምራለሁ … እፈትናለሁ፤* 11፥20፤ 12፥3 ይመ። *የአእምሮንም ሐሳብ፤* የዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም “ኵላሊት” ይላል (11፥20 ይመ)። የዕብራይስጡ ቃል በ12፥2 ላይ “ልብ” ተብሎ ተተርጒሞአል።

*17፥11፤* ነቢዩ የአሰበውን ነጥብ ለመግለጽ በምሳሌያዊ አነጋገር ተጠቅሞአል (በቍ9 እንዳደረገው ማለት ነው)፤ በተለይ ምሳ23፥5 ይመ። *ቆቅ፤* ይህች የአዕዋፍ ዘር በብሉይ ኪዳን ከዚህ ሌላ ተጠቅሳ የምትገኘው በ1ሳሙ26፥20 ላይ ብቻ ነው። *ያስፈለፈለችውን፤* ይህን አባባል ወክሎ የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ በሌላ ቦታ የሚገኘው በኢሳ34፥15 ላይ ብቻ ነው። ይሁን እንጂ ተቀራራቢ አባባል በኢል39፥14 ላይ ይገኛል። *በዕድሜው አጋማሽ፤* በዕብራይስጡ አባባል በቀጥታ ሲተረጐም፣ “በቀኖቹ አጋማሽ ላይ” የሚል ነው (በመዝ102፥24 ላይ እንዳለው ነው)። *ሞኝነቱ፤* በሥነ ምግባርም ሆነ በመንፈሳዊ ነገር ያልታረመ ማለት ነው (የምሳ1፥7 ማብ ይመ)።

17፥12-18፤ ኤርምያስ በግሉ “ከተናዘዛቸው” ክፍሎች ይህ አራተኛው ነው።

17፥12 *የክብር ዙፋን፤* የ14፥21 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ6፥1 ይመ። ብዙውን ጊዜ እግዚአብሔር በቤተ መቅደሱ ውስጥ በነበረው የኪዳኑ ታቦት ላይ በሁለቱ ኪሩብ መካከል ዙፋን ላይ የሚቀመጥ መሆኑ ተገልጾአል (ለምሳሌ:-መዝ80፥1፤ 99፥1 ይመ)። *ከፍ ያለ፤* የጽዮን ተራራ፣ “ከፍ ያለው የእስራኤል ተራራ” በመባል ይታወቃል (ሕዝ20፥40)። *ከጥንት ጀምሮ፤* ገና ዘመን ሳይቈጠር እግዚአብሔር የቤተ መቅደሱ መትከያ ስፍራ እንድትሆን ጽዮንን መርጦአታል ማለት ነው (ዘፀ15፥17 ይመ)።

17፥13 *የእስራኤል ተስፋ፤* የ14፥8 ማብ ይመ። *ዐፈር፤* የዕብራይስጡ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ «መሬት» ማለት ነው፤ ይህም አንዳንድ ጊዜ የሙታንን ዓለም የሚያመለክት ነው (የመዝ61፥2 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም የኢዮ7፥21 ማብ ይመ)፤ አገላለጹ በሕይወት “መጽሐፍ ውስጥ ተጻፈ” የሚለው ሐረግ ተቃራኒ ነው (ዘፀ32፥32፤ ዳን12፥1 ይመ፤ በተጨማሪም መዝ69፥28 እና ማብ፤ ሉቃ10፥20፤ ራእ20፥12፤ 21፥27 ይመ)። *የሕይወትን ውሃ ምንጭ … ትተዋልና፤* ከ15፥18 ጋር ያገናዝቡ፤ የ2፥13 ማብ ይመ።

17፥14 *ፈውሰኝ፤* 15፥18፤ መዝ6፥2 ይመ። *አንተ ምስጋናዬ ነህ፤* “እኔ የማመሰግነው አንተን ነው” ማለትም ይቻላል (ዘዳ10፥21 ይመ)።

*17፥15፤* 20፥8 ይመ። የኤርምያስ ባላንጣዎች እርሱ የሐሰት ነቢይ እንደ ሆነ አድርገው ያስወሩበታል (በዘዳ18፥21-22 ይመ)። በዚህ ዐይነት መንገድ ስሙን ማጕደፍ የጀመሩት የይሁዳ ምድር (በ605 ዓ.ቅ.ክ. ከከርከሚሽ ጦርነት በኋላ)፣ በባቢሎናውያን ለመጀመሪያ ጊዜ ከመወረሯ በፊት መሆን አለበት (46፥2 ይመ)።

17፥16 *እረኛ፤* መሪነትን የሚያመለክት አባባል ነው (የ2፥8 ማብ ይመ)፤ በመሆኑም ኤርምያስ የነቢያቱን ሚና ያሳያል።

17፥17 *በመከራ ቀን፤* ቍ18፤ 15፥11 ይመ። *መሸሸጊያዬ፤* የ16፥19 ማብ ይመ።

17፥18 *አሳዳጆቼ፤* 15፥15 ይመ። *በእጥፍ ድርብ፤* 16፥18፤ ኢሳ40፥2 እና ማብ ይመ።

## ሰንበትን ማክበር

[19]እግዚአብሔር እንዲህ አለኝ፤ “ሂደህ የይሁዳ ነገሥታት በሚገቡበትና በሚወጡበት በሕዝቡ በር በሌሎቹም የኢየሩሳሌም በሮች ሁሉ ቁም፤ [20]እንዲህም በላቸው፤ ‘በእነዚህ በሮች የምትገቡ የይሁዳ ነገሥታት ሆይ፤ የይሁዳ ሕዝብና በኢየሩሳሌም የምትኖሩ ሁሉ፤ የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ:: [21]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ “በሰንበት ቀን ሸክም ተሸክማችሁ በኢየሩሳሌም በሮች እንዳታስገቡ ለራሳችሁ ተጠንቀቁ:: [22]አባቶቻችሁን እንዳዘዝኋቸው ሰንበትን አክብሩ እንጂ በሰንበት ቀን ከየቤታችሁ ሸክም ይዛችሁ አትውጡ፤ ምንም ሥራ አትሥሩ::” [23]እነርሱ ግን አልሰሙም፤ ልብም አላሉም፤ እንዳይሰሙና እንዳይገሠጹም ዐንገታቸውን አደነደኑ:: [24]ነገር ግን በጥንቃቄ ብትታዘዙኝ ይላል እግዚአብሔር፤ በሰንበትም ቀን በዚህች ከተማ በሮች ሸክም ይዛችሁ ባትገቡ፣ የሰንበትንም ቀን ምንም ሳትሠሩ ብትቀድሱት፣ [25]በዳዊት ዙፋን ላይ የሚቀመጡ ነገሥታትና መኳንንታቸው በዚህች ከተማ በሮች ይገባሉ፤ በፈረሶችና በሠረገሎች ተቀምጠው በይሁዳ ሰዎችና በኢየሩሳሌም ነዋሪዎች ታጅበው ይመጣሉ፤ ይህቺም ከተማ ለዘላለም የሰው መኖሪያ ትሆናለች:: [26]ሰዎች ከይሁዳ ከተሞች፣ ከኢየሩሳሌም ዙሪያ፣ ከብንያምም አገር፣ ከቈላውና ከደጋው አገር እንዲሁም ከኔጌብ የሚቃጠል መሥዋዕትና ሌላ መሥዋዕት፣ የእህል ቍርባን፣ ዕጣንና የምስጋና መሥዋዕት ይዘው ወደ እግዚአብሔር ቤት ይመጣሉ:: [27]ነገር ግን የሰንበትን ቀን ሳትቀድሱ፣ በሰንበት ቀን ሸክም ተሸክማችሁ በኢየሩሳሌም በሮች በመግባት ትእዛዜን ብትጥሱ፣ በኢየሩሳሌም በሮች ላይ ምሽጎቿን የሚበላ፣ የማይጠፋ እሳት እጭራለሁ::”

## በሸክላ ሠሪው ቤት

**18** ከእግዚአብሔር ወደ ኤርምያስ እንዲህ የሚል ቃል መጣ:- [2]“ተነሥተህ ወደ ሸክላ ሠሪው ቤት ውረድ፤ በዚያ መልእክቴን እሰጥሃለሁ::” [3]እኔም ወደ ሸክላ ሠሪው ቤት ወረድሁ፤ ሸክላውንም በመንኰራኩር ላይ ይሠራ ነበር:: [4]ከጭቃ ይሠራው የነበረውም ሸክላ በእጁ ላይ ተበላሸ፤ ሸክላ ሠሪውም በሚፈልገው ሌላ ቅርጽ መልሶ አበጀው::

[5]የእግዚአብሔርም ቃል ወደ እኔ እንዲህ

17፥19 ኤር7፥2፤ 26፥2
17፥20 ኤር19፥3፤ 22፥2
17፥21 ዘኍ15፥32-36፤ዘዳ5፥14፤ነህ13፥15-21፤ዮሐ5፥10
17፥22 ዘፍ2፥3፤ ዘፀ20፥8፤ኢሳ56፥2-6
17፥23 2ዜና28፥22 ፤ኤር7፥26:28፤19፥15 ፤ዘካ7፥11
17፥24 ቍ 22
17፥25 2ሳሙ7፥13 ፤ኢሳ9፥7፤ኤር22፥2:4 ፤30፥10፤33፥16፤ሕዝ 28፥26ሉቃ1፥32
17፥26 ኤር32፥44፤ 33፥13፤ዘካ7፥7
17፥27 1ነገ9፥6፤ 2ነገ25፥9፤ነህ10፥31 ፤ኤር7፥20፤22፥5፤ ሆሴ8፥14፤አሞ2፥5

*17፥19-27፤* ክፍሉ የሚያተኵረው ሰባተኛውን ቀን (ሰንበትን) ስለ ማክበር በተሰጠው ትእዛዝ ላይ ነው፤ ይህ ትእዛዝ እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር የገባውን ኪዳንና በመካከላቸው ያለውን ግንኙነት የሚያመለክት ነበር (ዘፀ31፥13-17፤ ሕዝ20፥12 ይመ)፤ ምናልባትም በዘዳ5፥12-15 ላይ ያለውን በተለይ ይመለከታል (የቍ22 ማብ ልብ ይበሉ)::

17፥19 *በሕዝቡ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ አባባል ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “በሕዝቡ ልጆች” የሚል ሲሆን፣ በ26፥23፤ በ2ነገ23፥6 ላይ እንዲሁም በ2ዜና35፥5:7 ላይ፣ “ተራው ሕዝብ” ተብሎ ተተርጕሞአል:: እዚህ ላይ ያለው አገባብም አጠቃላይ ሕዝቡን የሚያመለክት እንደ መሆኑ፣ ሕዝብ በብዛት የሚሰበሰብበት የቤተ መቅደሱ ምሥራቅ በር መሆን አለበት፤ ነገሥታትም በዚሁ በር መውጣት መግባት ነበረባቸው::

17፥20 *የይሁዳ ነገሥታት፤* በዚህ ጊዜ ሥልጣን ላይ የነበረውንና ቀጥለው የተነሡትን ከዳዊት ሥርወ መንግሥት የነገሡትን የሚያመለክት ነው (ለምሳሌ:- ቍ25፤ 1፥18፤ 2፥26፤ 13፥13፤ 19፥3 ይመ)::

17፥21 *ተጠንቀቁ፤* ኢሱ 23፥11 ይመ:: ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ በዘዳ4፥15፣ “እጅግ ተጠንቀቁ” ተብሎ ተተርጕሞአል፤ በሚል2፥15 ላይ ደግሞ፣ “መንፈሳችሁን ጠብቁ” ተብሎአል፤ ይህም የእግዚአብሔር ትእዛዝ ብርቱና ክቡር መሆኑን አጽንዖት ለመስጠት ነው::

17፥22 *አትውጡ፤* የ16፥2 ማብ ይመ:: በአሉታዊ መልክ የተሰጠው ይህ ትእዛዝ በዕብራይስጡ አገባብ በቍ21 ላይ ከተሰጠው ጠንከር ያለ ነው:: *ሰንበትን አክብሩ እንጂ ... ምንም ሥራ አትሥሩ፤* በዘፀ20፥8:10፤ በዘዳ5፥12:14 ላይ የተሰጠውን ሰንበትን የማክበር ትእዛዝ በቀጥታ የሚጠቅስ ነው:: *እንዳዘዝኋቸው፤* በአጽንኦት የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ በአሪት ዘዳግም ዐሠርቱ ትእዛዛት ላይ ብቻ ሰፍሮ የሚገኘው ነው (ዘዳ5፥12:15-16 ይመ፤ የቍ19-27 ማብ ይመ)::

17፥23 *አልሰሙም ... አንገታቸውን አደነደኑ፤* ከ7፥26 እንዳለ የተጠቀሰ ነው (የዚያን ቍጥር ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 11፥10 ይመ):: *እንዳይሰሙና እንዳይገሠጹ፤* 2፥30፤ 5፥3 ይመ::

*17፥25፤* እዚህ ቍጥር ላይ የሚገኘው ሐሳብ በከፊል በ22፥4 ላይ ተደግሞአል:: የንጉሥ ዳዊት ሥርወ መንግሥት ለዘላለም ጸንቶ የሚኖር ነው (23፥5-6፤ 30፥9፤ 33፥15፤ 2ሳሙ7፥12-17 ይመ)፤ ኢየሩሳሌምም ምን ጊዜም መኖሪያ ሆና ከትውልድ ትውልድ ትዘልቃለች (ዘካ2፥2-12፤ 8፥3፤ 14፥11)፤ ይህም የሚሆነው የይሁዳ ሕዝብ ለእግዚአብሔር ታዛዥ ሆነው ሲገኙ ነው (ቍ27 ይመ)፤ በ31፥33-34 መሠረትም ሕዝቡ ታዛዥ ይሆናል::

17፥26 *ከብንያምም አገር፤* የኤርምያስ የትውልድ ስፍራም እዚያ ነበር (1፥1 ይመ):: *ከቈላውና ከደጋው አገር፤* ቈላ የተባለው “ምዕራባዊው የኰረብቶች ግርጌ”፣ ደጋው የተባለው ደግሞ “ኰረብታው አገር” ተብሎ ሊጠራ ይችላል፤ የዘዳ1፥7 ማብ ይመ:: *ከኔጌብ፤* የዘፍ12፥9 ማብ ይመ:: *የምስጋና መሥዋዕት፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ሐረግ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “የምስጋና መሥዋዕት በማምጣት” ይላል፤ ‘ይዘው’ ከሚለው ቃል በተጨማሪ ‘ማምጣት’ አብሮ ገብቶ ይታያል:: ይህም የሚያሳየው የምስጋና መሥዋዕት ከተዘረዘሩት ሌሎች መሥዋዕቶች በተለየ መንገድ ትኵረት እንደ ተሰጠውና ሌሎቹም መሥዋዕቶች ከምስጋና ጋር የተያያዙ መሆናቸውን ነው (በ33፥11 እንደተመለከተው ማለት ነው)::

*17፥27፤* አለመታዘዝ የእግዚአብሔርን ቍጣ ከማስከተሉም በላይ፣ በቍ24-26 ላይ የተሰጡትን የተስፋ ቃላት (ለጊዜውም ቢሆን) ሊያስቀር ይችላል:: *በኢየሩሳሌም በሮች፤* ሰንበትን አለማክበር ለቅጥሯ መውደም መንሥኤ ይሆናል፤ ሰንበት የማክበርን ትእዛዝ ጥሰው በበሯ ቢወጡ ቢገቡ፣ መውጫ መግቢያቸው ይፈርስባቸዋል:: *ምሽጎቿን የሚበላ ... እሳት እጭራለሁ፤* በዐመፀኛ ከተሞች ላይ የሚደርሰውን የእግዚአብሔር ቍጣ ለመግለጽ የተለመደ የነቢያት አባባል ነው (49፥27፤ 50፥32፤ አሞ 1፥4:7:10:12:14፤2፥2:5፤ ይመ፤ ከኤር21፥14 ጋር ያነጻጽሩ)::

*18፥1-20፥18፤* እነዚህ ሦስት ምዕራፎች እግዚአብሔር ኤርምያስን በሸክላ ሠሪው ቤት ባስተማረው ትምህርቶች ላይ ያተኵራሉ፤ ይህም የሆነው ከ605 ዓ.ቅ.ክ በፊት ይመስላል (የ17፥15 ማብ ይመ)::

*18፥1-17፤* ሸክላ ሠሪው የሸክላውን ጭቃ እንደ ፈለገው ማድረግ እንደሚችል፣ እግዚአብሔርም በይሁዳ ሕዝብ ላይ ሙሉ ባለሥልጣን ነው::

18፥2 *ውረድ፤* የሸክላ ሠሪው ቤት ምናልባት በሄኖም ልጅ ሸለቆ መውረጃ ላይ በ“ገልበር” አጠገብ ሳይሆን አይቀርም (19፥2 እና ማብ ይመ)::

18፥3 *መንኰራኵር፤* የዕብራይስጡ ቃል በቁሙ ሲተረጐም፣ “ሁለት ድንጋይ” የሚል ነው:: ሁለት መንኰራኵሮች ቀጥ ያለ ዘንግ ላይ ይሰኩና ሸክላ ሠሪው የታችኛውን መንኰራኵር በእግሩ እያዞረ የሚያበጀውን ሸክላ በላይኛው መንኰራኵር ላይ ያስተካክለዋል (ዘንጉ መሬት ውስጥ የተተከለ ነው)::

18፥4 *ተበላሸ፤* በ13፥7 ላይ የተጠቀሰው የበፍታ መቀነትም ከጥቅም ውጭ ሲሆን በዚሁ ቃል ተገልጾአል (የዚያኑ ክፍል ማብ ይመ):: *በሚፈልገው፤* ጕድለት ያለው ባለሙያው ሸክላ

ሲል መጣ፤ 6“የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ሸክላ ሠሪው እንደሚሠራው፣ እኔ በእናንተ ላይ መሥራት አይቻለኝምን?” ይላል እግዚ አብሔር፤ “የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ጭቃው በሸክላ ሠሪው እጅ እንዳለ፣ እናንተም እን ዲሁ በእጄ ውስጥ ናችሁ:: 7አንድ ሕዝብ ወይም መንግሥት እንዲነቀል፣ እንዲፈር ስና እንዲጠፋ በተናገርሁ ጊዜ፣ 8ያስጠነቀ ቅሁት ሕዝብ ከክፋቱ ቢመለስ፣ እኔ ላደ ርስበት ያሰብሁትን ክፉ ነገር እተዋለሁ:: 9በሌላም ጊዜ አንድን ሕዝብ ወይም መን ግሥት አንጸውና እተክለው ዘንድ ተና ግሬ፣ 10በፊቴ ክፉ ነገር ቢያደርግና ባይታ ዘዘኝ፣ አደርግለታለሁ ብዬ ያሰብሁትን መል ካም ነገር አስቀርበታለሁ::

11“አሁንም እንግዲህ ለይሁዳ ሕዝብና በኢ የሩሳሌም ለሚኖሩ እንዲህ በላቸው፤ ‘*እግ ዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “እነሆ፤ ጥፋ ትን እያዘጋጀሁላችሁ ነው፤ ክፋትንም እየጠነ ሰስሁላችሁ ነው:: ስለዚህ ሁላችሁ ከክፉ መንገዳችሁ ተመለሱ፤ መንገዳችሁንና ተግባ ራችሁን አቅኑ::”’ 12እነርሱ ግን፣ ‘በከንቱ አትድከም፤ ባቀድነው እንገፋበታለን፤ እያን ዳንዳችንም የክፉ ልባችንን እልኸኝነት እን ከተላለን’ ይላሉ::”

13ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

“እስቲ አሕዛብን፣
‘እንዲህ ዐይነት ነገር በመካከላችሁ
ተሰምቶ ያውቃል?’ ብላችሁ ጠይቁ::
ድንግሊቱ እስራኤል፣
እጅግ ክፉ ነገር አድርጋለች::
14የሊባኖስ ተራራ ድንጋያማ ተረተር፣
በረዶ ተለይቶት ያውቃልን?
ከጋራው የሚወርደውስ ቀዝቃዛ ውሃ፤
መፍሰሱን ያቋርጣልን?[ጠ]
15ሕዝቤ ግን ረስቶኛል፤
ለማይረቡ ነገሮች ዐጥኖአል፣በራሱ
መንገድ፣
በቀደሞው ጐዳና ተሰናክሎአል፤
በሻካራው መሂጃ፣
ባልቀናውም ጥርጊያ መንገድ ሄዶአል::
16ምድራቸው ባድማ፣
ለዘላለም መሣለቂያ ይሆናል፤
በዚያ የሚያልፍ ሁሉ ይደነቃል፤
በመገረምም ራሱን ይነቀንቃል::
17ከምሥራቅ እንደሚወጣ ነፋስ፣
በጠላቶቻቸው ፊት እበትናቸዋለሁ፤
በመጥፊያቸው ቀን፣
ጀርባዬን እንጂ ፊቴን አላሳያቸውም::”

18እነርሱም፣ “ሕግ ከካህናት፣ ምክር ከጠ ቢባን፣ ቃልም ከነቢያት ስለማይታጣ ኑና በኤርምያስ ላይ እንማከር፤ ኑ፤ በአንደበ ታችን እናጥቃው፣ እርሱ የሚናገረውንም ሁሉ አንስማ” አሉ::

19*እግዚአብሔር* ሆይ፤ ስማኝ፤
ባላንጣዎቼ የሚሉትን አድምጥ::

18፥6 ዘፍ2፥7፤ ኢሳ 29፥16፤45፥9፤ሮሜ 9፥20-21፤
18፥7 ኤር1፥10
18፥8 ዘፀ32፥14፤ መዝ25፥11፤ኤር 26፥13፤31፥28፤ 36፥3፤42፥10፤ዳን 9፥14፤ሆሴ11፥8-9፤ ኢል2፥13፤ዮና3፥8-10 ፤4፥2
18፥9 ኤር1፥10፤ 31፥28
18፥10 1ሳሙ2፥29 -30፤13፥13፤ኤ1፥10 ፤ሕዝ33፥18
18፥11 ቊ18፤ዘዳ4 4፥30፤2ነገ17፥13፤22 ፥16፤ኢዮ16፥17፤ኢሳ 1፥16-19፤ኤር4፥6፤ 7፥3
18፥12 ኢሳ57፥10፤ ኤር3፥17
18፥13 2ነገ19፥21 ፤ኢሳ66፥8፤ኤር5፥30
18፥15 ኢሳ1፥13፤ 17፥10፤57፥14፤62፥ 10፤ኤር6፥16፤10፥15 ፤44፥15:19፤51፥18፤ ሕዝ44፥12፤ሆሴ11፥2 ፤ሚል2፥8
18፥16 ዘሌ26፥32፤ ዘዳ28፥37፤2ነገ19፥21 ፤ኢዮ16፥4፤መዝ22፥7 ፤ኤር19፥8፤25፥9፤ 42፥18፤ሰቆ1፥12፤ሕዝ 33፥28-29
18፥17 2ዜና29፥6፤ ኢዮ7፥10፤ኤር2፥27፤ 13፥24

[ጠ]14 በዕብራይስጡ የዚህ ዐረፍተ ነገር ትርጒም በግልጽ አይታወቅም

*ሠሪ* ዘንድ ሳይሆን፣ በራሱ በሸክላው ውስጥ ነበር::

18፥6 *ጭቃው ... እንዳለ፣ እናንተም እንዲሁ ... ናችሁ፤* መጽሐፍ ቅዱስ ብዙውን ጊዜ፣ ሰውን ሸክላ ሠሪ እንደ ሠራው ሸክላ አድርጎ ይገልጠዋል (ኢዩ4፥19 እና ማብ ይመ):: *ሸክላ ሠሪው፤* ለተመሳሳይ ሐረግ የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል በ10፥16 ላይ እግዚአብሔርን ለማመልከት «ፈጣሪ» በሚል ቃል ተተርጒሞአል::

*18፥7-10፤* እግዚአብሔር ከሁሉ በላይ ሥልጣን ቢኖ ረውም፣ ሰው ከታዘዘውና ከኀጢአቱ ከተመለሰ ይቅር ሊለው ሊባ ርከው፣ እምቢ ካለና ካልታዘዘ ደግሞ ፍርድንና ጥፋትን ሊያስ ከትልበት በሰው ነጻ ምርጫ ላይ የመደገፍ አግራጭ እንዳለው ይገልጻል:: *ቢ(መለስ) ... ቢያደርግና ... ፤* የእግዚአብሔር የተስፋ ቃልና ማስጠንቀቂያው የሰውን ተግባር ይመረኰዛሉ:: የማ ይለወጠው እግዚአብሔር (ዘሌ23፥19፤ ሚል3፥6፤ ያዕ1፥17 ይመ) እንደ ሰው አቀባበል ሁኔታ በሰው ላይ ይፈጸም ዘንድ አስቀድሞ የተነገረውን ይለውጣል (የ4፥28 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢል 2፥13፤ ዮና3፥9 እና ማብ፤ ዮና3፥8-4፥2፤ 4፥11 ይመ)::

18፥7 *እንዲነቀል፣ እንዲፈርስና እንዲጠፋ፤* 1፥10 እና ማብ ይመ::

*18፥8፤* 26፥3 ይመ:: *ከክፋቱ ... ክፉ ነገር፤* በዕብራ ይስጥም የሁለቱ ሥርወ ቃል አመጣጥ አንድ ነው (በቍ11 ላይም)::

18፥9 *አንጸውና እተክለው፤* 1፥10 እና ማብ ይመ::

18፥11 *እየጠነሰስሁላችሁ፤* አስ8፥3፤ 9፥25፤ ሕዝ38፥10 ይመ:: *ከ... ተመለሱ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል በቍ8 ላይም “ቢመለስ” ተብሎ ተተርጒሞአል::

18፥12 *በከንቱ አትድከም፤* 2፥25 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ57፥10 ማብ ይመ:: *እያንዳንዳችንም የክፉ ልባችንን እልኸኝነት እንከተላለን፤* የ3፥17 ማብ ይመ::

*18፥13-17፤* 2፥10-13 ይመ::

18፥13 *ድንግሊቱ እስራኤል፤* 14፥17 እና ማብ ይመ:: *ክፉ ነገር፤* 5፥30፤ 23፥14፤ ሆሴ6፥10 ይመ::

*18፥14-15፤* ተፈጥሮ አስተማማኝ ብትሆንም (ቍ14)፣ ይሁዳ ተለዋዋጭና ከሓዲ ናት (ቍ15)::

18፥14 *የሊባኖስ፤* ከፍታው ከ10,000 ጫማ በላይ የሆነ፣ በሰሜኑ በኩል ከሚገኙት ትልልቅ ተራሮች አንዱ ነው (22፥6 ይመ)::

18፥15 *ሕዝቤ ... ረስቶኛል፤* 2፥32 ላይ ያለው ተድጋ ግሞአል (ያንኑ ማብ ይመ):: ዐጥኖአል፤ የ1፥16 ማብ ይመ:: *ለማ ይረቡ ነገሮች፤* የዕብራይስጡ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ “ከንቱ” የሚል ትርጒም አለው (መዝ31፥6 ይመ):: ለዚህ የገባው የዕብራ ይስጥ ቃል በ2፥5 ወይም በ2፥8 ላይ ከሚገኘው የተለየ ነው (የ2፥8 ማብ ይመ):: *ተሰናክሎአል፤* 2ዜና 28፥23 ይመ:: *በቀድ ሞው ጐዳና፤* የ6፥16 ማብ ይመ:: *ባልቀናውም ጥርጊያ መንገድ፤* የኢሳ35፥8 ማብ ይመ::

18፥16 *ባድማ ... ይደነቃል፤* በዕብራይስጡ ለእነዚህ የገቡት ቃላት ከተመሳሳይ ሥርወ ቃል የወጡ ናቸው:: *መሣለቂያ፤* 19፥8፤ 25፥9:18፤ 29፥18፤ 51፥37 ይመ:: ይህ ቃል ድንጋጤን፣ ማሾፍን ወይም ማቃለልን ለመግለጽ ማፍዋጨትን ያመለክታል:: *ሁሉ ይደነቃል፤* 19፥8፤ 1ነገ9፥8 ይመ:: *ራሱን ይነቀንቃል፤* 48፥27፤ ኢዮ16፥4 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም መዝ44፥14፤ 109፥25 ይመ::

18፥17 *ከምሥራቅ እንደሚወጣ ነፋስ፤* የ4፥11 ማብ ይመ፤ በተጨማሪ መዝ48፥7 ይመ:: *ጀርባዬን እንጂ ፊቴን አላሳያቸውም፤* ሕዝቡ ራሱ በእግዚአብሔር ላይ እንዳደረገው ማለት ነው (2፥27 ይመ):: ፊቱ የበረከትና የሞገስ ትእምርት ነው (ዘኍ6፥24-26 ይመ)::

*18፥18-23፤* ከኤርምያስ “የኑዛዜ” ክፍሎች ይህ አምስተ ኛው ነው::

18፥18 *እነርሱም፤* የኤርምያስ ባላንጣዎች ናቸው (የ17፥15 ማብ ይመ):: *በኤርምያስ ላይ እንማከር፤* ቍ12፤ 11፥18-23፤ 12፥6፤ 15፥10-11: 15-21 ይመ:: *ሕግ ከካህናት፤* ሕ ጉን ማስተማር የካህናት ተግባር ነበር (የዘዳ31፥11 ማብ ይመ):: *ከካህናት ... ከጠቢባን ... ከነቢያት፤* 8፥8-10 ይመ፤ በተጨ ማሪም ሕዝ7፥26 ይመ (በአብዛኛው ጥቅስ ላይ ‘ጠቢባን’ በሚ ለው ምትክ ‘ሽማግሌዎች’ ተብሎአል):: *በአንደበታችን እናጥ ቃው፤* የ9፥3 ማብ ይመ::

[20]የመልካም ተግባር ወሮታው ክፉ ነውን?
እነርሱ ግን ጕድጓድ ቈፈሩልኝ፤
ቍጣህን ከእነርሱ እንድትመልስ፣
በፊትህ ቆሜ ፣
ስለ እነርሱ እንደ ተናገርሁ አስብ።
[21]ስለዚህ ልጆቻቸውን ለራብ፣
ለሰይፍም ስለት አሳልፈህ ስጥ፤
ሚስቶቻቸው የወላድ መካን፣ መበለትም ይሁኑ፤
ወንዶቻቸው በሞት ይቀሠፉ፤
ጕልማሶቻቸው በጦር ሜዳ ለሰይፍ ይዳረጉ።
[22]ሊይዙኝ ጕድጓድ ስለ ቈፈሩ፣
ለእግሮቼም በስውር ወጥመድ ስለ ዘረጉ፣
በድንገት ወራሪ ስታመጣባቸው፣
ከቤታቸው ጩኸት ይሰማ።
[23]አንተ ግን እግዚአብሔር ሆይ፤
ሊገድሉኝ ያሴሩብኝን ሴራ ሁሉ ታውቃለህ፤
በደላቸውን ይቅር አትበል፤
ኀጢአታቸውንም ከፊትህ አትደምስስ፤
በፊትህ ወድቀው የተጣሉ ይሁኑ፤
በቍጣህም ጊዜ አትማራቸው።

**19** እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ሂድህ፣ ከሸክላ ሠሪ ገምቦ ግዛ፤ ከሕዝቡና ከካህናቱ መካከል ታላላቅ የሆኑትን አንዳንዶቹን ይዘህ፣ [2]በገል በር መግቢያ አጠገብ ወዳለው ወደ ሄኖም ልጅ ሸለቆ ውጣ፤ በዚያም የምነግርህን ቃል ተናገር፤ [3]እንዲህም በል፤ 'የይሁዳ ነገሥታትና በኢየሩሳሌም የምትኖሩ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ፤ የእስራኤል አምላክ የሠራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ለሰሚው ሁሉ ጆሮ የሚዘገንን ክፉ ነገር እነሆ በዚህ ስፍራ አመጣለሁ፤ [4]እኔን ትተውኛል፣ ይህን ስፍራ የባዕድ አማልክት ቦታ አድርገው ታልና። እነርሱም ሆኑ አባቶቻቸው፣ የይሁዳ ነገሥታትም ለማያውቋቸው አማልክት ሠውተዋል፤ ይህንም ስፍራ በንጹሐን ደም ሞልተውታል፤ [5]እኔም ያላዘዝኋቸውን፣ ያልተናገርኋቸውን፣ ፈጽሞም ያላሰብሁትን፣ ወንዶች ልጆቻቸውን በእሳት ሊሠውለት ለበአል መስገጃ ኰረብታዎች ሠርተዋል። [6]ስለዚህ ሰዎች ይህን ስፍራ የዕርድ ሸለቆ እንጂ፣ ከእንግዲህ ቶፌት ወይም የሄኖም ልጅ ሸለቆ ብለው የማይጠሩበት ዘመን ይመጣል፤ ይላል እግዚአብሔር።

[7]" 'በዚህ ስፍራ የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን ዕቅድ አፈርሳለሁ፤[ω] በጠላቶቻቸው ፊት ሕይወታቸውን በሚሹት እጅ በሰይፍ እንዲወድቁ አደርጋለሁ፤ ሬሳቸውንም ለሰማይ ወፎችና ለምድር አራዊት ምግብ አደርጌ እሰጣለሁ። [8]ይህችን ከተማ ድምጥማጧን አጠፋለሁ፤ ለመሣለቂያም አደርጋታለሁ፤ በዚያም የሚያልፉ ሁሉ ከደረሰባት

[ω]7 *አፈርሳለሁ* የሚለው የዕብራይስጡ ቃል አነባበብ *ገንቦ* ከሚለው ጋር ይመሳሰላል (ቍ1እና 10 ይመ)።

18፥18 ቍ11፤ኢዮ 5፥13፤መዝ52፥2፤ 64፥2-8፤ኤር2፥8፤ 5፥13፤9፥3፤11፥19፤ ሕዝ7፥26፤ሐጌ2፥11፤ ሚል2፥7
18፥19 መዝ71፥13
18፥20 ዘፍ20፥7፤ 44፥4፤ዘጸ9፥19፤መዝ 35፥7፤57፥6፤106፥23 ፤119፥85፤ኤር14፥7-9፤15፥1
18፥21 1ሳሙ15፥ 33፤መዝ63፥10፤ 109፥9፤ኢሳ9፥17፤ 47፥9፤ኤር11፥22፤ 14፥16፤ሰቆ 5፥3
18፥22 መዝ35፥15 ፤119፥85፤140፥5፤ኤር5፥26፤6፥26፤20፥10
18፥23 ነህ4፥5፤መዝ 59፥5፤ኤር10፥24፤ 11፥21፤37፥15
19፥1 ዘኍ11፥17፤ 1ነገ8፥1፤ኤር18፥2
19፥2 ኢሱ 15፥8
19፥3 1ሳሙ3፥11፤ ኤር17፥20፤ 6፥19
19፥4 ዘፀ20፥3፤ዘሌ 18፥21፤ዘዳ31፥16፤ 2ነገ21፥16፤ኢሳ 65፥11፤ ኤር1፥16
19፥5 ዘሌ18፥21፤ 2ነገ3፥27፤መዝ106፥ 37-38፤ኤር7፥31፤ሕዝ 16፥36
19፥6 ኢሱ15፥8፤ 2ነገ23፥10፤ኤር7፥32
19፥7 ቍ9፤ዘሌ

18፥20 *የመልካም ... ወሮታው ክፉ፤* መዝ35፥12 ይመ። *ጕድጓድ ቈፈሩልኝ፤* ጠላቶቹ በእርሱ ላይ ያሤሩትን የሚገልጥ አባባል ነው (ቍ22፤ መዝ57፥6 እና ማብ፤ ምሳ22፥14፤ 23፥27 ይመ)። *በፊትህ ቆሜ፤* የ51፥1 ማብ ይመ። *ስለ እነርሱ እንደ ተናገርሁ፤* 14፥7-9፡21 ይመ።

18፥21 *ለሰይፍም ስለት አሳልፈህ ስጥ፤* ለዚህ ሐረግ የገባው የዕብራይስጡ አቻ በመዝ63፥10፤ በሕዝ35፥5 ላይም ይገኛል። *በሞት ይቀሠፉ፤* በዕብራይስጥ ቋንቋ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "በሞት ይታረዱ" የሚል ነው፤ ምናልባትም ቸነፈርን ለማመልከት፣ በ15፥2 ላይ ባለው መልክ ገብቶ ሊሆን ይችላል (የዚያኑ ማብ ይመ)።

*18፥22-23፤* መዝ141፥8-10 ይመ።

18፥22 *በስውር ወጥመድ፤* መዝ140፥5፤141፥8-10 ይመ።

18፥23 *እግዚአብሔር ሆይ፣ ... ታውቃለህ፤* 12፥3፤ 15፥15 ይመ። *በደላቸውን ይቅር አትበል ... በፊትህ ወድቀው የተጣሉ ይሁኑ፤* ይህ ጸሎት ከግል የበቀል ፍላጎት የመነጨ ሳይሆን፣ የእግዚአብሔርን ቅን ፍርድ ከመሻት የተነሣ የቀረበ ጥሪ ነው።

*19፥1-15፤* ኤርምያስ ሆን ብሎ የሰበረው ገምቦ (ቍ1-10) ሊመጣ ያለውን የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን መጥፋት የሚያመለክት ነው (ቍ11-15)። በምዕ18 ላይ የሸክላው ጭቃ እርጥብና እንደ ፈለጉት ሊጠፈጠፍ የሚቻል ነበር፤ በመሆኑም በፈለጉት ቅርጽ ደጋግሞ ማበጀት ጭቃው ገና እርጥብ በመሆኑ፣ ቅርጹን ማስተካከል ያስችላል፤ በዚህም መንገድ ተፈላጊውን ቅርጽ ማግኘት ይቻላል (18፥1-11 ይመ)። በምዕ19 ላይ ግን የሸክላው ጭቃ ደርቆ ጠንክሮአል፤ የተሠራው ገምቦ ሊያገለግል ካልቻለ፣ ያለው ምርጫ ሰባብሮ መጣል ብቻ ነው (ቍ11ይመ)።

19፥1 *ገምቦ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል፣ ዕቃው ቀጠን ያለ አንገት ያለውና መጠኑ አነስተኛ እንደሆነ ያመለክታል። *ታላላቅ የሆኑትን፤* የዘፀ3፥16 ማብ ይመ። *ከሕዝቡና፤* 1ነገ8፥1-3 ይመ። *ከካህናቱ፤* 2ነገ19፥2 ይመ። በእስራኤል አገር የሽማግሌ ወገን በሁለት ቡድብ የተከፈለ ነበር፤ አንደኛው ወገን ማኅበራዊ ጕዳይን የሚፈጽም ሲሆን፣ ሌላው ወገን ደግሞ ሃይማኖት ነክ ተግባራትን የሚያከናውን ነበር።

19፥2 *ሄኖም ልጅ ሸለቆ፤* የ7፥31 ማብ ይመ። *በገል በር፤* "ገል" ለሚለው የገባው የዕብራይስጡ ቃል "ሸክላ" ተብሎ በቍ1 ላይ ከተጠቀሰው ቃል ጋር አንድ ዐይነት ነው። ይህ 'የገል በር' የተባለው ስፍራ፣ ወደ ኢየሩሳሌም ከሚያስገቡት የቅጥር በሮች አንዱ ሲሆን፣ በነህ2፥13 (የዚህን ማብ ይመ)። 3፥13-14፤ 12፥31 ላይ "የጕድፍ መጣያ በር" ከተባለው በር አንድ እንደ ሆነ አንዳንድ የአይሁድ የብሉይ ኪዳን ትርጕሞች ይናገራሉ፤ የገል በር የተባለበት ምክንያትም በበሩ ትይዩ፣ የሸክላ ስባሪ መጣያ ስፍራ ስለ ነበር ነው።

19፥3 *ነገሥታት፤* የ17፥20 ማብ ይመ። *ለሰሚው ... ጆሮ የሚዘገንን ክፉ ነገር፤* በ2ነገ21፥12 ላይ ካለው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይ ነው (1ሳሙ3፥11 ይመ)። አገላለጹ ስለ አንድ አሥጊ ሁኔታ በተነገረ ጊዜ፣ የሚመጣውን የድንጋጤ ስሜት የሚያመለክት ነው።

19፥4 *እነርሱም፤* ባዕድ አምልኮን ከእውነተኛው አምላክ አምልኮ ጋር ያጣመሩትን ሁሉ ማለት ነው። *ይህን ... ቦታ፤* ኢየሩሳሌምን ነው። *ሠውተዋል፤* ለዚህ ሐረግ የገባው የዕብራይስጡ ቃል "ዕጣን ማጠን" ተብሎ በዚሁ በኤርምያስ መጽሐፍ ላይ ተተርጕሞአል። (የ1፥16 ማብ ይመ)። *ይህንም ስፍራ በንጹሐን ደም ሞልተውታል፤* የእግዚአብሔርን ሰዎች ደም ለማለት ነው (2፥34፤ 7፥6፤ 22፥3፡17፤ 26፥15 ይመ)፤ በተለይም ንጉሥ ምናሴ በጭካኔ ያፈሰሰው ዐይነት ማለት ነው (15፥4 እና ማብ ይመ፤ በተለይም 2ነገ21፥16 በተጨማሪ ይመ)።

*19፥5-6፤* ከ7፥31-32 ተደጋግሞ የተጠቀሰ ነው (የዚያኑን ማብ ይመ)።

19፥7 *አፈርሳለሁ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ "አፈሳለሁ" የሚል ነው (የቍ1 ማብ ይመ)፤ የዚሁ ቃል ድምፀት፣ "ገምቦ"ን ከሚተካው የዕብራይስጥ ቃል ጋር ተመሳሳይ ነው። ኤርምያስ ይህን በሚናገርበት ጊዜ ምናልባት ከገምቦው ውሃ እያፈሰሰ ሊሆን ይችላል (ከ2ሳሙ 14፥14 ጋር ያነጻጽሩ)። *በጠላቶቻቸው ፊት ... በሰይፍ እንዲወድቁ፤* ባቢሎናውያን የእግዚአብሔር የመቅጫ በትር ናቸው (20፥6 ይመ)። *ሬሳቸውንም ... ለምድር አራዊት ምግብ፤* የ7፥33 ማብ ይመ።

*19፥8፤* በ18፥16 ላይ የተነገረውን አባባል ያንጸባርቃል (የዚያን ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ሕዝ27፥35፤ ሶፎ2፥15 ይመ)። *ለመሣለቂያም ... ያሾፉሉም፤* በዕብራይስጡ እንዚህም ከአንድ

ጕዳት የተነሣ ወይ ጕድ! ይላሉ ያሾፉሉም። [9]የወንዶችና የሴቶች ልጆቻቸውን ሥጋ እንዲበሉ አደርጋለሁ፤ ሕይወታቸውን ለማጥፋት የሚሹ ጠላቶቻቸው ከበው ሲያስጨንቋቸው፣ አንዱ የሌላውን ሥጋ ይበላል።'

[10]"ገምቦውንም ከአንተ ጋር በሄዱ ሰዎች ፊት ትሰብራለህ፤ [11]እንዲህም ትላቸዋለህ፤ 'የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "የሸክላ ሠሪው ገንቦ እንደ ተሰበረና ሊጠገን እንደማይቻል፣ ይህን ሕዝብና ይህቺን ከተማ እንዲሁ እሰብራለሁ፤ የቀብር ቦታ ከመታጣቱ የተነሣ ሙታናቸውን በቶፌት ይቀብራሉ። [12]በዚህ ስፍራና በውስጡም በሚኖሩት ላይ ይህን አደርጋለሁ፤ ይላል *እግዚአብሔር*። ይህቺን ከተማ እንደ ቶፌት አደርጋታለሁ። [13]በጣራዎቻቸው ላይ ለሰማይ ሰራዊት ዕጣን የታጠነባቸውና ለባዕዳን አማልክት የመጠጥ ቍርባን የቀረበባቸው፣ የኢየሩሳሌም ቤቶችና የይሁዳ ነገሥታት ቤቶች እንደ ቶፌት የረከሱ ይሆናሉ።

[14]ኤርምያስም *እግዚአብሔር* ትንቢት እንዲናገር ልኮት ከነበረበት ከቶፌት ተመልሶ፣ *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ አደባባይ በመቆም፣ ለሕዝቡ ሁሉ እንዲህ አለ፤ [15]"የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'እነሆ ዐንገታቸውን በማደንደን ቃሌን ስላልሰሙ በዚህች ከተማና በዙሪያዋ ባሉ መንደሮች ሁሉ ላይ ላደርስ ያሰብሁትን ጥፋት ሁሉ አመጣለሁ።" '

26፥17፤ዘዳ28፥25:26፤መዝ33፥10-11፤ኤር16፥4፤34፥20
19፥8 ዘሌ26፥32፤ ዘዳ28፥37፤29፥22፤ ኤር18፥16፤25፥9፤ሰቆ2፥15-16
19፥9 ቍ7፤ዘሌ26፥ 29፤ዘዳ28፥49-57፤ኤር21፥7፤34፥20፤ሰቆ4፥10
19፥10 ቍ1፤መዝ2፥9፤ኤር13፥14
19፥11 መዝ2፥9፤ ኢሳ30፥14፤ኤር7፥32
19፥13 ዘዳ4፥19፤ 2ነገ17፥16፤23፥12፤ ኢዮ38፥32፤መዝ74፥7፤ኢሳ57፥6፤ ኤር8፥2፤32፥29፤ 52፥13፤ሕዝ16፥41፤ 20፥28፤ሐሥ7፥42
19፥14 2ዜና20፥5፤ ኤር7፥2፤26፥2
19፥15 ቍ3፤ነህ 9፥16፤ኤር11፥11፤ 22፥21፤ሐሥ7፥51
20፥1 2ነገ25፥18፤ 1ዜና24፥14፤ሉቃ 22፥52
20፥2 ዘዳ25፥2-3፤ ኢዮ29፥7፤13፥27፤ ኤር 1፥19፤15፥15፤ 9፥26፤37፥13:15፤ 38፥7፤ዘካ14፥10፤

## ኤርምያስና ጳስኮር

**20** *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ውስጥ አለቃ የነበረው፣ የኢሜር ልጅ ካህኑ ጳስኮር እነዚህን ነገሮች ኤርምያስ እንደ ተነበየ በሰማ ጊዜ፣ [2]ነቢዩ ኤርምያስን መታው፣ *በእግዚአብሔርም* ቤተ መቅደስ በላይኛው የብንያም በር በእግር ግንድ ጠረቀው። [3]በማግስቱም ጳስኮር ኤርምያስን ከተጠረቀበት ግንድ አወጣው፤ ኤርምያስም እንዲህ አለው፤ "*እግዚአብሔር* ከእንግዲህ ማጎርሚሳቢብ[a] ብሎ ይጠራሃል እንጂ ጳስኮር አይልህም፤ [4]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ 'አንተንና ባልንጀሮችህን ሁሉ ለሽብር እዳርጋለሁ፤ የገዛ ዐይንህ እያየ በጠላቶቻቸው ሰይፍ ይወድቃሉ። ይሁዳን ሁሉ ለባቢሎን ንጉሥ አሳልፌ እሰጣለሁ፤

ሐሥ16፥24፤2ቆሮ11፥24፤ዕብ11፥36 20፥3 ቍ10፤መዝ31፥13፤ ሆሴ1፥4 20፥4 ኤር13፥19፤21፥10፤25፥9፤29፥21፤39፥9፤52፥27

[a]3 *ማጎርሚሳቢብ ማለት ዙሪያ-ገባው ሽብር ማለት ነው*

*ሥርወ ቃል የተገኙ ናቸው። ወይ ጕድ! ይላሉ፤* ሁለቱም በዕብራይስጡ ከአንድ ሥርወ ቃል የተገኙ ናቸው።

*19፥9፤* ኪዳኑን ካለመጠበቅ የተነሣ ሊመጡ ከሚችሉት የእርግማን ዐይነቶች አንዱ ነው (ዘሌ 26፥29፤ ዘዳ 28፥53-57 ይመ)። *የወንዶችና የሴቶች ልጆቻቸውን ሥጋ እንዲበሉ ... አንዱ የሌላውን ሥጋ ይበላል፤* ኢየሩሳሌም በባቢሎናውያን በ586 ዓ.ቅ.ክ ተከባ፣ ምግብ ከኩተማዪቱ ጨርሶ በጠፋ ጊዜ፣ ሰው ሰውን በልቶአል (ሰቆ2፥20፤ 4፥10፤ ሕዝ5፥10 ይመ)። ይህ ዘግናኝ ድርጊት በእስራኤል አገር ያልተለመደ ነው ማለት አይቻልም (2ነገ6፥28-29 ይመ)፤ እንደ ገናም ደግሞ በ70 ዓ.ም ሮማውያን ኢየሩሳሌምን በከበቡ ጊዜ ይኸው ድርጊት ተፈጽሞአል (ዘካ11፥9 እና ማብ ይመ)።

19፥11 *የሸክላ ሠሪው ገምቦ እንደ ተሰበረና ... ይህን ሕዝብና ... እሰብራለሁ፤* ተሠርቶ ያበቃለት ሸክላ ከደረቀ በኋላ ቢሰበር መልሶ መጠገኑ ይከብዳል፤ ይህም የሚያሳየው በኢየሩሳሌምና በይሁዳ ላይ የተላለፈው ፍርድ ምን ያህል የከፋ እንደ ሆነ ነው፤ ሆኖም እግዚአብሔር ከምሕረቱ የተነሣ የእስራኤልን ሕዝብ፣ ዛሬም ቢሆን ያለ ትሩፍ አልተወውም (ኢሳ1፥9 ይመ)። *ሊጠገን እንደማይቻል፤* የቍ1-15 ማብ ይመ።

19፥13 *እንደ ቶፌት የረከሱ ይሆናሉ፤* ንጉሥ ኢዮስያስ ቀደም ብሎም ቶፌትን 'ርኩስ አድርጎአል' (2ነገ23፥10)። *በጣራዎቻቸው ላይ፤* 32፥29 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ15፥3 ማብ ይመ። *ዕጣን የታጠነባቸውና፤* የ1፥16 ማብ ይመ። የይሁዳ ነገሥታት በኢየሩሳሌም በነበሩ አብያተ መንግሥቶቻቸው ጣራ ላይ፣ የአረማውያንን መሠዊያዎች አሠርተው ነበር (2ነገ23፥12 ይመ)። *ለሰማይ ሰራዊት፤* ፀሓይን፣ ጨረቃንና ከዋክብትን ማምለክ በይሁዳ ዘንድ እንደ ነበረ፣ ወደ ኋላ ከተነሡት ነገሥታታቸው ታሪክ መገንዘብ ይቻላል (ለምሳሌ:- 2ነገ17፥16፤ 21፥3:5፤ 23፥4-5፤ ሶፎ1፥5 ይመ)። *ለባዕዳን አማልክት የመጠጥ ቍርባን፤* የ7፥18 ማብ ይመ።

19፥14 *ለሕዝቡ ሁሉ፤* በቍ1 ላይ ከተጠቀሱት የካህናት ታላላቆች ቍጥር ላቅ ያለውን ብዙ ሕዝብ የሚያመለክት ነው።

19፥15 *በዙሪያዋ ባሉ መንደሮች፤* በአስተዳደርና በኤኮኖሚ በኢየሩሳሌም ላይ ተደጋፊ የሆኑ የይሁዳ ከተሞችን ያመለክታል (1፥15፤ 9፥11 ይመ)። *ዐንገታቸውን በማደንደን ቃሌን ስላልሰሙ፤* በ7፥26 ላይ ካለው አባባል ጋር ተመሳሳይ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 11፥10 ይመ)።

*20፥1-6፤* ኤርምያስ እግዝዚአብሔር ያዘዘውን የሸክላ ሠሪውን ምሳሌ ባሳየ ጊዜ፣ ጳስኮር በድርጊት የገለጸው ምላሽ በቍ1-2 ላይ ሲጠቀስ፣ ኤርምያስ ለዚሁ የሰጠው ምላሽ ደግሞ በቍ3-6 ላይ ሰፍሮ ይገኛል።

20፥1 *ጳስኮር፤* በ21፥1፤ 38፥1 ላይ አንድ ወይም ከዚያ በላይ የሆኑ ሰዎች በዚህ ስም ተጠርተዋል። *ኢሜር፤* ምናልባት በኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ የ16ኛው የካህናት ተራ (ምድብ) ኀላፊ (አለቃ ) የነበረው ሰው (1ዜና24፥14 ይመ) ዝርያ ሊሆን ይችላል። *አለቃ፤* በነበረው አሠራር፣ ችግር ፈጣሪ የሆኑ ሰዎችን በቤተ መቅደሱ አደባባይ የመቅጣት ሥልጣን የነበረው ካህን ነው፤ የችግር ፈጣሪዎቹ ሁኔታ ቢጣራም ባይጣራም፣ ይዞ መቅጣት መብቱ ነበር (ቍ2፤ 29፥26 ይመ)። በሥልጣን ተዋረድ ከእርሱ በላይ ያለው ሹም የካህናት አለቃው ብቻ ነበር (29፥25-26 እና 52፥24ን ያነጻጽሩ)። በቤተ መቅደሱ ውስጥ ሕግና ሥርዐት መከበሩን የሚቈጣጠረውም እርሱ ነው (ከሉቃ 22፥52፤ ከሐሥ4፥1፤ 5፥24 ጋር ያነጻጽሩ)።

*20፥2፤* በኤርምያስ አካል ላይ ከደረሱትና ከተመዘገቡት ብዙ የሥቃይ ዐይነቶች ይህ የመጀመሪያው ነው። *ነቢዩ፤* ኤርምያስ በመጽሐፉ ውስጥ በዚህ ማዕረግ ሲጠራ የመጀመሪያ ጊዜ ነው፤ እዚህ ላይ የገባበት ዐላማም የጳስኮርን መዳፈር ለመግለጽ ነው። *መታው፤* ምናልባት ይህን ያደረገው የሙሴን ሕግ መሠረት አድርጎ ይሆናል (ዘዳ25፥2-3፤ የዘዳ25፥3 ማብ ይመ)። *በእግር ግንድ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ አቻ፣ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ማዕቀብ፣ ግዞት" ማለት ነው (በ2ዜና16፥10 ላይ ደግሞ "ግዞት" ተብሎ ተተርጕሞአል)። *በላይኛው የብንያም በር፤* ምናልባት፣ "በሰሜን በኩል ያለው የውስጠኛው አደባባይ በር" ከሚለው ጋር አንድ ዐይነት ሊሆን ይችላል (ሕዝ8፥3፤ 2ነገ15፥35 ይመ፤ በተጨማሪም ሕዝ9፥2 ይመ)። *በእግዚአብሔርም ቤተ መቅደስ፤* ይህ ገላጭ ሐረግ ከከተማዋ የቅጥር በሮች አንዱ "የብንያም በር" በመባል ስለሚታወቅ (37፥13፤ 38፥7)፣ ወደ ቤተ መቅደሱ አደባባይ መግቢያ የሆነውን ይህኛውን በር "የብንያም በር" በማለት ከዚያኛው ለመለየት ነው። ሁለቱም በሮች በከተማዋ ሰሜናዊ ክፍል የሚገኙና ከብንያም ምድር ትይዩ የሆኑ ነበሩ።

20፥3 *ማጎርሚሳቢብ፤* የስሙ ትርጕም፣ "ሽብር ከየአቅጣጫው" ማለት ነው፤ በተጨማሪም የ6፥25 ማብ ይመ። "ዙሪያ ገባው ሽብር" የሚለው ሐረግ (ቍ10 ይመ) በሰቆ2፥22 ላይ በብዙ ቍጥር ተገልጦአል።

*20፥4፤* አዲሱ የጳስኮር ስም በመላው የይሁዳ ምድር ሽብር እንደሚመጣ የሚያመለክት ነው፤ ሕዝቡ ይማረክና ተግዞ ወደ ባቢሎን ምድር ይወሰዳል፤ አለዚያም በገዛ ምድሩ ይገደላል። *ባልንጀሮችህን፤* ቃል የተገባቡ ግብረ አበሮችን ያመለክታል (ቍ6 ይመ)። *ለባቢሎን ንጉሥ፤* በ605 ዓ.ቅ.ክ. የነገሠው ናቡከ ደንፆር

እርሱም ወደ ባቢሎን ያፈልሳቸዋል፤ በሰይፍም ይገድላቸዋል። [5]የዚህችን ከተማ ሀብት ሁሉ፣ ጥሪቷን፣ የይሁዳን ነገሥታት ውድ ዕቃና ንብረት ሁሉ ለጠላቶቻቸው አሳልፌ እሰጣለሁ፤ እነርሱም ዘርፈው ወደ ባቢሎን ይዘውት ይሄዳሉ። [6]ጳስኮር ሆይ፤ አንተና በቤትህ የሚኖሩት ሁሉ ወደ ባቢሎን ትጋዛላችሁ። አንተና በሐሰት ትንቢት የተነበይህላቸው ባልንጀሮችህ በዚያ ትሞታላችሁ፤ በዚያም ትቀበራላችሁ።' "

## የኤርምያስ ማጕረምረም

[7]እግዚአብሔር ሆይ፤ አታለልኸኝ፤[a] እኔም ተታለልሁ፤
አንተ ከእኔ እጅግ በረታህ፤ አሸነፍህም፤
ቀኑን ሙሉ ማላገጫ ሆንሁ፤
ሁሉም ተዘባበቱብኝ።
[8]በተናገርሁ ቍጥር እጮኻለሁ፤
"ሁከትና ጥፋት!" ብዬ ዐውጃለሁ፤
ስለዚህ የእግዚአብሔር ቃል፣
ቀኑን ሙሉ ስድብና ነቀፋ
አስከተለብኝ።
[9]ነገር ግን፣ "ከእንግዲህ የእርሱን ስም
አላነሣም፤
በስሙም አልናገርም" ብል፣
ቃሉ በልቤ እንደ እሳት፣
በዐጥንቴም ውስጥ እንደ ረመጥ ሆነብኝ፤
ዐፍኜ መያዝ አቃተኝ፤
ጩርሶ መቋቋም አልቻልሁም።
[10]"በየቦታው ሽብር አለ፤
አውግዙት፤ እናውግዘው!"
ብለው ብዙ ሲያንሾካሽኩ ሰማሁ፤
መውደቄን በመጠባበቅ፣
ባልንጀሮቼ የነበሩ ሁሉ፣
"ይታለል ይሆናል፣
ከዚያም እናሸንፈዋለን፤
እንበቀለዋለንም" ይላሉ።
[11]ነገር ግን እግዚአብሔር እንደ ኀያል
ተዋጊ ከእኔ ጋር ነው፤
ስለዚህ አሳዳጆቼ ይሰናከላሉ እንጂ
አያሸንፉም፤
ክፉኛ ይዋረዳሉ እንጂ አይሳካላቸውም፤
ውርደታቸውም ከቶ አይረሳም።
[12]ጻድቁን የምትፈትን ልብንና አእምሮን
የምትመረምር፣
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ሆይ፤
ጉዳዬን ለአንተ አሳልፌ ሰጥቻለሁና
ስትበቀላቸው ለማየት አብቃኝ።
[13]ለእግዚአብሔር ዘምሩ፤
ለእግዚአብሔር ምስጋናን አቅርቡ፤
የችግረኛውን ነፍስ፣
ከክፉዎች እጅ ታድጎአልና።
[14]የተወለድሁባት ዕለት የተረገመች ትሁን፤
እናቴ እኔን የወለደችባት ቀን

20፥5 2ነገ20፥17፤ 25፥15፤ኤር17፥3
20፥6 ኤር14፥15፤ ሰቆ2፥14
20፥7 ዘፀ5፥23፤ 22፥16፤ኢዮ12፥4፤ 17፥2፤መዝ119፥21 ኢሳ8፥11፤አሞ3፥8፤ 1ቆሮ 9፥16
20፥8 2ዜና36፥16 ፤ኤር6፥7:10፤28፥8
20፥9 ኢዮ4፥2፤ መዝ39፥3፤ኤር4፥19 ፤6፥11፤44፥16፤አሞ 3፥8፤ሐሥ4፥20
20፥10 1ሳሙ18፥25፤1ነገ19፥2፤ነህ6፥6-13፤ኢዮ19፥14፤መዝ 57፥4፤ኢሳ29፥21፤ ኤር6፥25፤11፥19፤ 13፥21፤18፥22፤ሉቃ 11፥53-54
20፥11 መዝ129፥2 ፤ኤር1፥8፤7፥19፤15፥ 15፤17፥18፤23፥40፤ ሮሜ8፥31
20፥12 ዘዳ32፥35፤ መዝ7፥9፤62፥8፤ኤር 11፥20፤17፥10፤ሮሜ 12፥19
20፥13 መዝ34፥6፤ 35፥10፤97፥10፤ኢሳ 12፥6
20፥14 ኢዮ3፥8:16 ፤ኤር15፥10

[a]7 *ወይም ሐሳቤን አስለወጥኸኝ*

ነው (የ17፥15፤ 18፥1-20፥18 ማብ ይመ)።

*20፥5፤* በዚህ ቍጥር ላይ የተነገረው ቃል የተፈጸመው በ597 ዓ.ቅ.ል.ክ (2ነገ24፥13 ይመ)፣ እንዲሁም በ586ዓ.ቅ.ክ. (52፥17-23፤ 2ነገ25፥13-17 ይመ) ነበር።

20፥6 *ጳስኮር ሆይ፤ አንተና ... ትጋዛላችሁ፤* ምናልባት ይህ የሆነው በ597 ዓ.ቅ.ክ. ሳይሆን አይቀርም፤ ምክንያቱም ከዚያ ዓመት በኋላ ወዲያው (29፥2 ይመ) ሁለት ሰዎች በተከታታይ ጳስኮርን በመተካት የቤተ መቅደስ አለቆች ሆነዋል (29፥25-26 ይመ)። *በሐሰት ትንቢት የተነበይህላቸው፤* ካህኑ ጳስኮር በማስመሰል ነቢይ ለመሆን ሞክሮ ነበር።

*20፥7-18፤* ይህ ክፍል፣ የመጨረሻውና ረዥሙ የኤርምያስ "ኑዛዜ" የሚገኝበት ነው። በአንዳንድ ነጥቦችም ከሌሎቹ ይበልጥ ድፍረትና መራርነት የሞላበት ነው።

*20፥7፤* ከ15፥18 ጋር ያነጻጽሩ። *አታለልኸኝ፤* የዕብራይስጡ አቻ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ "በማባበል ማሳሳት" (ዘፀ 22፥16) ወይም "በማስጕምጀት ማሳት" (1ነገ22፥20-22) ማለት ይሆናል፤ ቍ10 ይመ። ኤርምያስ፣ እግዚአብሔር መጀመሪያውኑ ነቢይ አድርጎ ሲያቆመው፣ በመገፋፋትና በማባበል እንደ ጠራው ይታወቃል (1፥7-8:17-19 ይመ፤ ከሕዝ14፥9 ጋር ያነጻጽሩ)።

*20፥8፤* ኤርምያስ መከራ የተቀበለው ስለ እግዚአብሔር ሲል ብቻ እንደ ሆነና እግዚአብሔር በሕይወቱ ለመጠቀም ስለ ፈለገ እንደ ነበር ይናገራል። *ሁከትና ጥፋትን፤* የነቢዩ መልእክት የሚያንጸባርቀው የእግዚአብሔርን ቃል ነው (6፥7 ይመ)። *ነቀፋ፤* መዝ44፥13፤ 79፥4 ይመ።

*20፥9፤* የአንድ ነቢይ ማንነራገር በመለኮታዊ ግፊት ድል ሲነሣና አለመታዘዙ ሲረታ የሚያሳይ ጊዜ የማይሽረው አገላለጽ ነው (1፥6-8፤ አሞ3፥8 ይመ፤ ከሐሥ4፥20፤ ከ1ቆሮ9፥16 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቃሉ ... እንደ እሳት፤* 5፥14፤ 23፥29 ይመ። ይህን ዐይነት አገላለጽ የተጠቀመበት ነቢዩ ኤርምያስ ብቻ ነው (በተጨማሪም ሰቆ1፥13 ይመ)።

*20፥10፤* በዕብራይስጡ፣ በዚህ ቍጥር ላይ ያለው ግጥም የመጀመሪያዎቹ ሁለት መስመሮች ከመዝ31፥13 የመጀመሪያዎቹ ሁለት ቍጥሮች ጋር አንድ ዐይነት ናቸው። *በየቦታው ሽብር፤* የ6፥25 ማብ ይመ። ይህ አባባል እዚህ ላይ የሚያገለግለው ለኤርምያስ የቅጽል ስም በመሆን ነው፤ ይኸውም የእርሱ መልእክት የሚያስደነግጥና የሚያሳዝን በመሆኑ ነው። *መውደቄን በመጠባበቅ፤* መዝ35፥15፤38፥16 ይመ። *ባልንጀሮቼ፤* ለዚህ ቃል የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ "የሰላሜ/ የበጎነቴ ሰዎች" የሚል ነው፤ ተመሳሳዩ የዕብራይስጥ ቃል መዝ41፥9 ላይ ይገኛል። *ይታለል ...፤* ቍ7 እና ማብ ይመ። *እናሸንፈዋለን፤* እንዳሉት ይሆናል ማለት ሳይሆን፣ ጠላቶቹ እንደዚያ እንበረታብታለን ብለው ያስባሉ (ቍ11 ይመ)። *እንበቀለዋለንም፤* የፈለገውን ያህል ቢሆን፣ ጠላቶቹ እንዲህ በቀላሉ የሚተውት አልነበሩም (11፥19፤ 12፥6፤ 26፥11 ይመ፤ ከመዝ56፥5-6፤ 71፥10 ጋር ያነጻጽሩ)።

20፥11 *እግዚአብሔር ... ከእኔ ጋር ነው፤* 1፥8 እና ማብ ይመ። *ኀያል፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል በ15፥21 "ጨካኝ" ተብሎ ተተርጕሞአል፤ እዚያ ላይ የተበቀለውም የኤርምያስን ጠላቶች ለመግለጽ ነው። እዚህ ላይ የሰፈረው ግን በዐውዱ መሠረት ለየት ያለ ትርጕም ይዞ ነው፤ አገባቡም "ጭካኔን" ሁሉ ድል ለማድረግ ሥልጣንና ኀይል ያለው እግዚአብሔር መሆኑን ለማሳየት ነው። *ተዋጊ፤* የዘፀ14፥14፤ 15፥3 ማብ ይመ።

*20፥12፤* 11፥20 ላይ ያለው አብዛኛው ተደግሞአል።

20፥13 *ዘምሩ ... ምስጋናን አቅርቡ፤* 31፥7 ይመ፤ በተጨማሪም ለመዝ9 የተጻፈውን መግቢያ ይመ። *ከክፉዎች እጅ ታድጎአልና፤* 15፥21፤ 21፥12 ይመ። *የችግረኛውን፤* 22፥16 ይመ። በኤርምያስ ዘመን፣ "ድኻ/ ችግረኛ" የተባሉት ቃላት በብዙ ረገድ "ጽድቅ" የሚለውን ትርጕም እንዲያዝሉ ሆነዋል (አሞ2፥6 ይመ፤ በተጨማሪም የመዝ9፥18፤ 34፥6 ማብ ይመ)።

*20፥14-18፤* ኢዮ3፥3-19 ይመ። ኤርምያስ በደስታ ከፍ ካለበት ከፍታ (ቍ13) አሁን ቍልቍል ተስፋ ወደ መቍረጥ አዘቅት ሲወርድ እናያለን። የማይታጠፈው መለኮታዊ ጥሪ (ቍ9)፣ የባለንጀሮቹ ክሕደት (ቍ10)፣ ጠላቶቹ ያለ ርኅራኄ ማሳደዳቸው (ቍ7:11) እንዲሁም የመልእክቱ አሉታዊና ኩናኝ መሆን (ቍ8) ይህ ሁሉ በአንድነት ተዳምሮ አስገራሚ የትካዜና ተስፋ የመቍረጥ ቃላት ከአንደበቱ እንዲወጡ አስገድዶታል። በተጨማሪም ይህ ክፍል ወደሚቀጥለው ታላቅ የመጽሐፉ ክፍል መሸጋገሪያ ነው። የይሁዳና የኢየሩሳሌም መጥፋት አይቀሬ መሆኑን ኤርምያስ ቀጥሎ ያቀርባል (21፥1-10 ይመ)።

20፥14 *የተወለድሁባት ዕለት የተረገመች ትሁን፤* የኢዮ 3፥3 ማብ ይመ። ነቢዩ በመጀመሪያ የተቀበለው መለኮታዊ ጥሪ

አትባረክ::

[15]“ወንድ ልጅ ተወልዶልሃል” ብሎ፣
ለአባቴ የምሥራች የነገረ፣
ደስ ያሰኘውም ሰው የተረገመ ይሁን::
[16]ያ ሰው እግዚአብሔር ሳይራራ፣
እንደ ገለበጣቸው ከተሞች ይሁን፤
በማለዳ ዋይታን፣
በቀትርም የጦርነትን ውካታ ይስማ፤
[17]እናቴ መቃብር ትሆነኝ ዘንድ፣
ማሕፀንም ስፊ የዘላለም ማደሪያዬ እንዲ
ሆን፣
ከማሕፀንም ሳልወጣ አልገደለኝምና::
[18]ችግርና ሐዘንን ለማየት፣
ዘመኔንም በውርደት ለመፈጸም፣
ለምን ከማሕፀን ወጣሁ?

## ለንጉሥ ሴዴቅያስ የተሰጠ ምላሽ

**21** የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ፣ የመልክያን ልጅ ጳስኮርን እንዲሁም የመዕሤያን ልጅ ካህኑን ሶፎንያስን ወደ እርሱ በላከ ጊዜ፣ ቃል ከእግዚአብሔር ወደ ኤርምያስ መጣ፤ የተላኩትም እንዲህ ብለውት ነበር፤ [2]“የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር[a] ሊወጋን ስለሆነ፣ እባክህን ፈጥነህ እግዚአብሔርን ጠይቅልን፤ ምናልባት ንጉሡ ከእኛ ይመለስ ዘንድ እግዚአብሔር እንደ ቀድሞው ታምራት ያደርግልን ይሆናል” ብለው ነበር::

[3]ኤርምያስ ግን እንዲህ አላቸው፤ “ለሴዴቅያስ እንዲህ ብላችሁ ንገሩት፤ [4]‘የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ከቅጥሩ ውጭ የከበቡአችሁን የባቢሎንን ንጉሥና ባቢሎናውያንን[b] ለመውጋት በእጃችሁ የያዛችሁትን የጦር መሣሪያ በእናንተው ላይ አዞራለሁ፤ ወደዚህችም ከተማ ሰብስቤ አስገባቸዋለሁ:: [5]እኔ ራሴ ለቅጣት በተዘረጋ እጅና በብርቱ ክንድ፣ በቍጣና በመዓት፣ በታላቅም መቅሠፍት እወጋችኋለሁ:: [6]በዚህች ከተማ የሚኖሩትን፣ ሰዎችንም ሆኑ እንስሳትን እመታለሁ፤ እነርሱም በታላቅ መቅሠፍት ይሞታሉ:: [7]ከዚያ በኋላ፣ ይላል እግዚአብሔር፣ የይሁዳን ንጉሥ ሴዴቅያስንና መኳንንቱን፣ ከመቅሠፍት፣ ከሰይፍና ከራብ የተረፈውንም ሕዝብ ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደነፆርና ሕይወታቸውን ለማጥፋት ለሚሹ ጠላቶቻቸው አሳልፌ እሰጣለሁ፤ እርሱም በሰይፍ ይመታቸዋል፤ አያዝንላቸውም፤ አይራራላቸውም፤ አይምራቸውምም::’

20፥16 ዘፍ19፥25፤ ኤር 6፥26
20፥17 ኢዮ 3፥16፤ 10፥18-19
20፥18 ዘፍ3፥17፤ 1ነገ19፥4፤ኢዮ3፥10-11፤5፥7፤መዝ90፥9፤ 102፥3፤መክ4፥2
21፥1 2ነገ24፥18፤ 25፥18፤1ዜና9፥12፤ ኤር52፥1
21፥2 ዘፍ10፥10፤ 25፥22፤2ነገ22፥18፤ 25፥1፤መዝ44፥1-4፤ ኤር32፥17
21፥4 ኤር32፥5፤ 37፥8-10
21፥5 ዘፀ3፥20፤ኢሱ 10፥14፤2ነገ22፥13፤ ኤር6፥12፤ሕዝ 5፥8
21፥6 ኤር7፥20፤ 14፥12
21፥7 ዘሌ26፥17፤ 2ነገ25፥7፤2ዜና29፥ 19፤36፥17፤ኤር11፥ 21፤14፥12፤15፥5:9፤ 19፥9፤27፥6:8፤32፥4፤ 34፥3፤36፥10፤37፥17 ፤38፥18፤39፥5፤52፥9፤ ሕዝ7፥9፤12፥14፤ዕን 1፥6

[a]2 *ናቡከደነፆር* አቻ የሆነው የዕብራይስጡ *ናቡከደነፆር* በዚህ ክፍልና ብዙ ጊዜ በኤርምያስና ሕዝቅኤል መጽሐፍ ይገኛል

[b]4 ወይም *ከለዳውያን*፤ ቍ9 ላይ ይመ::

---

መሠረት አጠያያቂ ሆኖበታል (1፥5 ይመ)::

*20፥15፤* በጥንት ዘመን፣ “ወንድ ልጅ ተወለደልህ” መባል ትልቅ በረከት ነበር (ለምሳሌ:- ዘፍ29፥31-35 ይመ)፤ ኤርምያስ ግን የራሱን ልደት እንደ ርግማን ይቈጥራል:: *...ሰው የተረገመ ይሁን፤* ሰያፍ አነጋገር እንጂ ይህ አባባል በቀጥታ አንድን ሰው ለመርገም የተሰነዘረ አይደለም::

20፥16 *እግዚአብሔር ... እንደ ገለበጣቸው ከተሞች*፤ ሰዶምንና ገሞራን የሚያመለክት ነው (ዘፍ19፥24-25:29 ይመ):: በኤርምያስ ዘመን የሰዶምና የገሞራ ክፋት መተረቻ ከመሆን ደረጃ ደርሶ ነበር (23፥14፤ ዘዳ29፥23 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ 1፥9-10 ማብ ይመ):: *የጦርነትን ውካታ፤* 4፥19 ይመ:: *በቀትር*፤ የ6፥4 ማብ ይመ::

20፥17 *ሰፊ፤* የዕብራይስጡ ቃል፣ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “እርግዝ” የሚል ይሆናል:: ኤርምያስ በመከራ ውስጥ በመሆኑ፣ የተሸከመውና እንዲወለድ ምክንያት የሆነው የእናቱ ማሕፀን ለዘላለም መቀበሪያው ይሆን ዘንድ ሲመኝ ይታያል::

*21፥1-24፥10፤* ነቢዩ በዚህ ክፍል የይሁዳን ገዦች (21፥1-23፥7)፣ ሐሰተኞች ነቢያትንና (23፥8-40) ለኀጢአት ራሳቸውን አሳልፈው የሰጡትን ሰዎች (ም24) በግልጥ ይናገርባቸዋል፤ ይወቅሳቸዋል:: ከም1-20 ያለው የመጽሐፉ ክፍል በአብዛኛው የጊዜን ቅደም ተከተል ጠብቆ የቀረበ ሲሆን፣ ም21-52 ግን የጊዜ ቅደም ተከተልን ሳይሆን የትረካውን ርእስ ጕዳዮች በመከተል የቀረበ ነው (24፥1፤ 25፥1፤ 26፥1፤ 27፥1፤ 29፥2፤ 32፥1፤ 35፥1፤ 36፥1፤ 37፥1፤ 45፥1፤ 49፥34፤ 51፥59፤ 52፥4 ይመ)::

*21፥1-23፥7፤* ለአገር ኢኮኖሚያዊና ማኅበራዊ ችግሮች፣ እንዲሁም ለመንፈሳዊ ጕድለቶች ተቀዳሚ ኀላፊነት ያለባቸው የይሁዳ ገዦች፣ ለመጀመሪያ ጊዜ የተወቀሱት በኤርምያስ ነው::

21፥1 *ቃል ... መጣ፤* ይህ ሐረግ እንደ ገና የሚገኘው በ25፥1 ላይ ብቻ ነው፤ ይህም የሚያሳየው በም21-24 ላይ የሚገኘው ክፍል በኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ ራሱን የቻለ አንድ ወጥ መሆኑን ነው:: *ሴዴቅያስ*፤ የስሙ ትርጕም፣ “እግዚአብሔር ጽድቁ ነው” ማለት ነው:: *የመልክያን ልጅ ጳስኮር*፤ በ20፥1-6 ላይ ካለው ጳስኮር ጋር አንድ አይደለም (38፥1 ይመ):: *የመዕሤያ ልጅ ካህኑ ሶፎንያስ፤* ከነቢዩ ከሶፎንያስ ጋር አንድ አይደለም (29፥25:29፤ 37፥3፤ 52፥24 ይመ፤ በተጨማሪም ሶፎ1፥1 ይመ)::

21፥2 *ናቡከደነፆር*፤ የስሙ ትርጕም፣ “ናቡ (የጣዖት ስም) ሆይ፤ ልጄን ከልል/ጋርድ” ማለት ነው:: *እግዚአብሔርን ጠይቅልን፤* ሰዎቹ ለማግኘት የፈለጉት ዕውቀት ወይም መረጃ ይመስላል (ዘፍ25፥22፤ 2ነገ22፥13 ይመ)፤ ጥያቄው፣ እርዳታ ጥያቄ ነው ማለት አይቻልም:: በአዲሲቱ ባቢሎን ግዛት (612-539 ዓ.ቅ.ክ.) ከታወቁት ገዦች በላይ ዝነኛ ገዥ ነበር (605-562 ዓ.ቅ.ክ):: *ሊወጋን*፤ በ588 ዓ.ቅ.ክ አካባቢ ሳይሆን አይቀርም፤ ምክንያቱም አብሪተኛው ሴዴቅያስ በባቢሎን መንግሥት አገዛዝ ላይ ዐምፆ ነበር (52፥3 ይመ):: *ሊወጋን*፤ ኢየሩሳሌምን ሊወጋ ማለት ነው:: *እንደ ቀድሞው ታምራት ያደርግልን ይሆናል*፤ ለምሳሌ:- ያህል በሕዝቅያስ ዘመን እንዳደረገው ማለት ነው (ኢሳ37፥36 ይመ):: *ይመለስ ዘንድ፤* ኢሳ 37፥37 ይመ::

21፥4 *የጦር መሣሪያ በእናንተው ላይ አዞራለሁ፤* ኢየሩሳሌምን የምትከላከሉበት መከላከያ ይወድቃል ማለት ነው:: *ባቢሎናውያን*፤ ከለዳውያን በመባልም ይታወቃሉ፤ በተጨማሪም የኢዮ1፥17 ማብ ይመ:: *ወደዚህችም ከተማ ሰብስቤ አስገባቸዋለሁ*፤ ሁለት ትርጕም ሊኖረው ይችላል:- (1)መሣሪያው ሁሉ ማለትም የይሁዳ ሰራዊት፣ የከተማዋን አቅራቢያ ወይም ዙሪያ ገባውን ለመከላከል ዐቅም አይኖረውም ማለት ነው፤ (2)የኢየሩሳሌም መመታትና መያዝ በቅርቡ የሚፈጸምና አይቀሬ እንደ መሆኑ፣ ባቢሎናውያንን ሰብስቤ አመጣባችኋለሁ ማለት ሊሆን ይችላል::

21፥5 *እኔ ራሴ ... እወጋችኋለሁ፤* ከዚህ ቀደም የሕዝቡ ተሟጋችና ተከላካይ የሆነው እግዚአብሔር፣ አሁን ያጠፋቸዋል፤ ከቶ እንደማይተርፉም ያደርጋል:: *በተዘረጋ እጅና በብርቱ ክንድ*፤ 27፥5፤ 32፥17 ይመ:: እስራኤላውያን ከግብፅ በወጡ ጊዜም የእግዚአብሔርን የማዳን ኀይል ለመግለጽ ይኸው ተመሳሳይ ሐረግ ሰፍሮ ይገኛል (32፥21፤ ዘዳ4፥34፤ 5፥15፤ 7፥19፤ 26፥8 ይመ)፤ እዚህ ላይ ግን እግዚአብሔር ቍጣውን በገዛ ሕዝቡ ላይ ሲያወርድ ይታያል:: *በቍጣና በመዓት፣ በታላቅም መቅሠፍት*፤ ምናልባት ከዘዳ29፥28 የተጠቀሰ ሳይሆን አይቀርም::

21፥7 *ሴዴቅያስንና መኳንንቱን ... የተረፈውንም ሕዝብ ... አሳልፌ እሰጣለሁ፤* ይህ ትንቢት በ52፥8-11:24-27 ላይ ተፈጽሞአል (ሕዝ12፥13-14 ይመ):: *ከመቅሠፍት፣ ከሰይፍና ከራብ*፤ ቍ9 ይመ:: ስለነዚህ ሦስት ጣምራ ቃላት የ14፥12 ማብ ይመ:: *አያዝንላቸውም፤ አይራራላቸውም፤ አይምራቸውምም*፤ ስለነዚህ ሦስት ጣምራ ቃላት 13፥14 ይመ፤ በተጨማሪም ሕዝ5፥11 ይመ:: የሦስቱ ጣምራ ቃላት ሦስት ጊዜ በዚህ ክፍል መግባት፣ የክፍሉን የሥነ ጽሑፍ ደረጃ ከፍ ያደርገዋል::

⁸“በተጨማሪም ለዚህ ሕዝብ እንዲህ በል፤ ‘እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ እነሆ፤ የሕይወትን መንገድና የሞትን መንገድ በፊታችሁ አድርጌአለሁ፤ ⁹በዚህች ከተማ የሚቈይ ሁሉ በሰይፍ፣ በራብና በመቅሠፍት ይሞታል፤ ወጥቶ ለከበቧችሁ ባቢሎናውያን እጁን የሚሰጥ ግን ነፍሱን ያተርፋል፤ በሕይወትም ይኖራል። ¹⁰በዚህች ከተማ ላይ በጎ ሳይሆን ክፉ ለማድረግ ወስኛለሁ፤ ይላል እግዚአብሔር፤ ለባቢሎን ንጉሥ ትሰጣለች፤ እርሱም በእሳት ያጠፋታል።’

¹¹“ለይሁዳ ንጉሥ ቤትም እንዲህ በል፤ ‘የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ፤ ¹²የዳዊት ቤት ሆይ፤ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤’

“ ‘ካደረጋችሁት ክፋት የተነሣ፣
ቍጣዬ እንዳይቀጣጠል፣
ማንም ሊያጠፋው እስከማይችል
እንዳይነድ፣
በየማለዳው ፍትሕን አድርጉ፤
የተበዘበዘውን ሰው፣
ከጨቋኙ እጅ አድኑት።
¹³ከሸለቆው በላይ፣
በድንጋያማው ዐምባ ላይ የምትኖሪ
ሆይ፤
እኔ በአንቺ ላይ ወጥቻለሁ፤
ይላል እግዚአብሔር።
“ማን በእኛ ላይ ይወጣል?
ማንስ ወደ መኖሪያችን ደፍሮ
ይገባል?” የምትሉ ሆይ፤
¹⁴እንደ ሥራችሁ መጠን እቀጣችኋለሁ፤
ይላል እግዚአብሔር፤
በዱሯም እሳት እለኵሳለሁ፤
በዙሪያዋ ያለውንም ሁሉ ይበላል።

21፥8 ዘዳ 30፥15
21፥9 ኤር14፥12፤ 27፥11፡12፤38፥2፡17፤ 39፥18፤40፥9፤45፥5፤ ሕዝ 5፥12
21፥10 2ነገ25፥9፤ 1ዜና36፥19፤ኤር20፥4፤32፥28፤38፥2-3፤ 44፥11፡27፤አሞ9፥4
21፥11 ኤር13፥18
21፥12 ዘፀ22፥22፤ ዘሌ25፥17፤መዝ27፥11፤ኢሳ1፥31፤42፥25፤ ኤር10፥10፤23፥2
21፥13 2ሳሙ5፥6-7፤መዝ125፥2፤ኤር 23፥30፤49፥4፤50፥31 51፥25፤ሰቆ4፥12፤ሕዝ 5፥8፤13፥8፤21፥3፤ 29፥10፤34፥10፤አብ 1፥3-4፤ናሆ2፥13፤3፥5
21፥14 2ነገ19፥23፤ 2ዜና36፥19፤ምሳ1፥31፤ኢሳ3፥10-11፤ኤር 17፥10፤ሰቆ2፥3፤ሕዝ 20፥47
22፥1 ኤር13፥18፤ 34፥2
22፥2 ኤር17፥20፡ 25፤አሞ7፥16፤ሉቃ 1፥32
22፥3 ዘፀ22፥22፤ ዘሌ25፥17፤መዝ72፥4 ፤ኢሳ1፥17፤56፥1፤ኤር 5፥1፡28፤7፥6፤21፥12፤ ሕዝ33፥14፤45፥9፤ ሆሴ12፥6፤አሞ5፥24፤ ሚክ6፥8፤ዘካ7፥9
22፥4 ኤር17፥25

## በክፉዎች ነገሥታት ላይ የተሰጠ ፍርድ

**22** እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ “ወደ ይሁዳ ንጉሥ ቤተ መንግሥት ውረድ፤ ይህንም መልእክት በዚያ እንዲህ ብለህ ተናገር፤ ²‘በዳዊት ዙፋን የተቀመጥህ፣ የይሁዳ ንጉሥ ሆይ፤ አንተና መኳንንትህ፣ በእነዚህም በሮች የሚገባ ሕዝብህ፣ የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ። ³እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ “ፍትሕንና ጽድቅን አድርጉ፤ የተበዘበዘውን ከጨቋኙ እጅ አድኑት፤ መጻተኛውን፣ ወላጅ የሌለውንና መበለቲቱን አትበድሉ፤ አትግፏቸውም፤ በዚህም ስፍራ ንጹሕ ደም አታፍስሱ። ⁴እነዚህን ትእዛዛት በሚገባ ብትጠብቁ፣ በዳዊት ዙፋን ላይ የሚቀመጡ ነገሥታት፣ ከመኳንንታቸውና ከሕዝባቸው ጋር በሠረገሎችና በፈረሶች ተቀምጠው በዚህ ቤተ መንግሥት በሮች ይገባሉ፤ ይወጣሉም። ⁵ነገር ግን እነዚህን ትእዛዛት ባትጠብቁ፣ ይህ ቤተ መንግሥት እንዲወድም በራሴ ምያለሁ፤ ይላል እግዚአብሔር።’ ”

*21፥8-10፤* 27፥12-13 ይመ:: በ38፥2-3:17-18 ላይ ተመሳሳይ ማስጠንቀቂያ ያለበት ምክር ተሰጥቶአል (ዘዳ30፥15-20 ይመ)::

21፥8 *እነሆ፤ ... በፊታችሁ አድርጌአለሁ፤* ዘዳ11፥26 ይመ:: ሕዝቡ ምርጫ ተሰጥቶታል፤ ይሁን እንጂ ትክክለኛውን ውሳኔ የወሰነ አለ ለማለት አይቻልም:: *የሕይወትን መንገድና የሞትን መንገድ፤* ዘዳ30፥15:19 ይመ፤ በተጨማሪም ምሳ 6፥23 ይመ::

*21፥9፤* በ38፥2 ላይ እንዳለ ተደግሞአል ማለት ይቻላል:: በብዙዎቹ አመለካከት ኤርምያስ፣ ሕዝቡን እጅ እንዲሰጥ መምከሩ ከክህደት ያስቈጥረዋል ይላሉ (37፥13 ይመ)፤ ነገር ግን እርሱ ኢየሩሳሌም ከተያዘች በኋላ እንኳ ከይሁዳ ለመውጣት ያልፈለገ እውነተኛ አርበኛ ነበር (37፥14፤ 40፥6፤ 42፥7-22 ይመ):: *ለ ... ባቢሎናውያን እጁን የሚሰጥ ... ነፍሱን ያተርፋል፤* በ39፥9፤ 52፥15 ላይ ተፈጽሞአል:: *በሕይወትም ይኖራል፤* ለዚህ ሐረግ የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ “ነፍሱን (ብቻ) በምርኮ ያገኛል” የሚል ነው:: በጦርነት ድል የተቀዳጁ ምርኮን ለመካፈል ያስባሉ፤ ድል የተመቱት ግን ሕይወታቸው ስለ ተረፈ ዕድለኞች ናቸው::

21፥10 *ወስኛለሁ፤* የዕብራይስጡ ቃል በቀጥታ ሲተረጐም፣ “ፊቴን በ... ላይ አድርጌአለሁ” የሚል ነው (44፥11 ይመ):: *በጎ ሳይሆን ክፉ፤* አሞ9፥4 ይመ፤ ከ24፥6 ጋር ያነጻጽሩ:: *ለ ... ትሰጣለች፤ ... በእሳት ያጠፋታል፤* 34፥2 ይመ::

21፥12 *ፍትሕን አድርጉ፤* 5፥28፤ 22፥16፤ 1ነገ3፥28፤ ሰቆ 3፥59 ይመ:: ንጉሡ ይህን እንዲያደርግ ግዴታው ነው፤ ይጠበቅበታልም፤ ወደ ፊት የሚመጣው መሲሕም እንዲሁ ፍትሕን ያሰፍናል (23፥5፤ 33፥15 ይመ):: *በየማለዳው፤* የሰው አእምሮ ብሩህ በሆነበትና ጊዜውም ቀዝቀዝ ባለበት ሁኔታ ማለት ነው (ችሎት የሚካሄደው በውጭ ከከተማው መግቢያ ላይ ነበር፤ የዘፍ19፥1፤ የሩት4፥1 ማብ ይመ):: *የተበዘበዘውን ... አድኑት፤* በ22፥3 ተደግሞ ይገኛል:: *ቍጣዬ ... ማንም ሊያጠፋው እስከማይችል፤* ከ4፥4 እንዳለ ቃል በቃል ተደግሞአል (አሞ5፥6 ይመ):: *ቍጣዬ እንዳይቀጣጠል፤* ኀ5፥4፤ 17፥4:27 ይመ::

21፥13 *ከሸለቆው፤* በሦስት አቅጣጫ በሸለቆ የተከበበችው ኢየሩሳሌም (የኢሳ22፥7 ማብ ይመ) በኢሳ22፥1:5 ላይ “የራእይ ሸለቆ” ተብላ ተጠርታለች:: *በድንጋያማው ዐምባ፤* የጽዮን ተራራ ማለት ነው:: *የምትሉ ሆይ፤* የጥቅሱ ሁለተኛ አጋማሽ በብዙ ቍጥር የቀረበ ሲሆን (የኢየሩሳሌምን ነዋሪዎች በማመልከት)፣ የመጀመሪያው አጋማሽ ግን በነጠላ ቍጥር የቀረበ ነው (ኢየሩሳሌም ራሷ በሰውኛ ዘይቤ ተገልጣለች):: *ማን በእኛ ላይ ይወጣል?* ማንም ወገን ቢሆን፣ ሙሉ በሙሉ ተሳክቶለት እነርሱን የሚከባቸው አልመሰላቸውም (የ7፥4፤ የ8፥19 ማብ ይመ)::

21፥14 *እንደ ሥራችሁ መጠን፤* የ17፥10 ማብ ይመ:: *እሳት እለኵሳለሁ፤ ... ይበላል፤* የ17፥27 ማብ ይመ:: *በዱሯም፤* በኢየሩሳሌም የነበረውን ቤተ መንግሥት በዘይቤአዊ አነጋገር የሚገልጽ ሳይሆን አይቀርም፤ ይኸውም በኢየሩሳሌም የነበረው ቤተ መንግሥት፣ “የሊባኖስ ዱር ቤተ መንግሥት” ተብሎ ይጠራ ስለ ነበር ነው (1ነገ7፥2፤ 10፥17-21፤ ኢሳ22፥8 ይመ)፤ ይህም የሆነበት፣ ቤተ መንግሥቱ በሚሠራበት ጊዜ ከዚያ አገር የመጣ ዝግባ በብዛት ጥቅም ላይ ስለ ዋለ ነው (22፥7:14:15:23 ይመ):: ቤተ መንግሥቱ (22፥1 ይመ) በ22፥6 ላይ “ከሊባኖስ ተራራ ጫፍ” ጋር ተነጻጽሮአል (22፥23 ይመ፤ በዚሁ ቍጥር ‘ሊባኖስ’ የተባለው በኢየሩሳሌም የነበረው ቤተ መንግሥት መሆኑንም ያስተውሉ)::

22፥1 *ውረድ፤* ቤተ መንግሥቱ፣ ከቤተ መቅደሱ ዝቅ ያለ ስፍራ ላይ እንደ ነበር ያመለክታል (26፥10፤ 36፥10-12 ይመ)::

22፥2 *የይሁዳ ንጉሥ፤* ምናልባት ሴዴቅያስ (21፥3:7 ይመ፤ ቍ3 ከ21:12 ጋር ያነጻጽሩ) ከእርሱ ቀደም ብለው የነበሩ ነገሥታት ቅደም ተከተላቸውን ጠብቀው፣ በዚህ ምዕራፍ ውስጥ ተጠቅሰዋል (ኢዮስያስ ቍ10:15-16፤ ኢዮአክስ/ ሰሎም ቍ10-12፤ ኢያአቄም ቍ13-15:17-19፤ ኢዮአኪን/ ኢኮንያን ቍ24-30):: *በዳዊት ዙፋን፤* ከዳዊት ሥርወ መንግሥት የተነሡት ሁሉ፣ ይነስም ይብዛ ጕድለት ነበረባቸው፤ ሆኖም ድል አድራጊው መሲሕ አንድ ቀን የዳዊት ሥርወ መንግሥት ቍንጮ ሆኖ ይገለጣል (23፥5፤ 33፥15፤ ሕዝ 34፥23-24፤ ማቴ1፥1 ይመ):: *በእነዚህም በሮች የሚገባ፤* 17፥25 እና ማብ ይመ::

*22፥3፤* ኢሳ11፥3-5 ከሕዝ22፥6-7 ጋር ያነጻጽሩ::

*22፥4፤* በከፊል ከ17፥25 የተደገመ ነው::

*22፥5፤* 17፥27 እና ማብ ይመ:: *በራሴ ምያለሁ፤* የዘፍ 22፥16፤ የኢሳ45፥23 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 49፥13፤ 51፥14 ይመ:: ከ44፥26 ጋር ያነጻጽሩ:: *እንዲወድም፤* በ52፥13 ተፈጽሞ

[6]ስለዚህ *እግዚአብሔር* ስለ ይሁዳ ንጉሥ ቤተ መንግሥት እንዲህ ይላል፤

"አንተ ለእኔ እንደ ገለዓድ፣
እንደ ሊባኖስ ተራራ ጫፍ ውብ
ብትሆንም፣
በእርግጥ እንደ ምድረ በዳ፣
ሰው እንደማይኖርባቸው ከተሞች
አደርግሃለሁ::
[7]በነፍስ ወከፍ መሣሪያ የሚይዙትን፣
አጥፊዎችን በአንተ ላይ አዘጋጃለሁ::
ምርጥ የዝግባ ዛፎችን ይቈርጣሉ፤
ወደ እሳትም ይጥሏቸዋል::

[8]"ከተለያየ አገር የመጡ ሕዝቦች በዚህች ከተማ በኩል ሲያልፉ፣ '*እግዚአብሔር* በዚህች ታላቅ ከተማ ላይ ለምን እንዲህ አደረገ?' እያሉ እርስ በርስ ይነጋገራሉ፤ [9]ከዚያም፣ 'የስምምነታቸውን *የእግዚአብሔርን* ኪዳን ትተው ሌሎችን አማልክት ስላመለኩና ስላገለገሉ ነው' ይላሉ::"

[10]ከእንግዲህ ስለማይመለስ፣
የተወለደባትንም ምድር ዳግመኛ
ስለማያይ፣
ለተማረከው ንጉሥ አምርራችሁ አልቅሱ
እንጂ፣
ቀድሞ ለሞተው አታልቅሱ፤ አትዘኑም::

[11]በአባቱ ምትክ በይሁዳ ላይ ስለ ነገሠው፣ ከዚህ ስፍራ በምርኮ ስለ ተወሰደው፣ ስለ ኢዮሲያስ ልጅ ስለ ሰሎ[T] *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ "ከእንግዲህ አይመለስም፤ [12]ተማርኮ በሄደበት አገር ይሞታል እንጂ ይህቺን ምድር ዳግመኛ አያይም::"

[13]"ቤተ መንግሥቱን በግፍ ለሚሠራ፣
ሰገነቱንም ፍትሕ በማዛባት ለሚገነባ፣
ወገኑን በነጻ ለሚያሠራ፣
የድካሙንም ዋጋ ለማይከፍለው፣
[14]'ባለ ትልልቅ ሰገነት፣
ሰፊ ቤተ መንግሥት ለራሴ እሠራለሁ'
ለሚል ወዮለት!
ሰፋፊ መስኮቶችን ያበጅለታል፤
በዝግባ እንጨት ያስጌጠዋል፤
ቀይ ቀለምም ይቀባዋል::

[15]"በዝግባ ዕንጨት ብዛት፣
የነገሥህ ይመስልሃልን?
አባትህስ ፍትሕንና ጽድቅን በማድረጉ፣
የሚበላውና የሚጠጣው ጐድሎት ነበርን?
እነሆ፣ ሁሉም መልካም ሆነለት::
[16]የድኾችንና የችግረኞችን ፍትሕ
አላጓደለም፤
ስለዚህም ሁሉ መልካም ሆነለት::
እኔን ማወቅ ማለት ይህ አይደለምን?"
ይላል *እግዚአብሔር::*
[17]"የአንተ ዐይንና ልብ ያረፉት ግን፣
አጭበርብሮ ጥቅምን በማግኘት፣
የንጹሑን ደም በማፍሰስ፣
ጭቈናንና ግፍን በመሥራት ላይ ብቻ
ነው::

22፥5 ዘፍ22፥16፤ ኤር17፥27፤ዕብ6፥13
22፥6 ዘፍ31፥21፤ 1ነገ7፥2፤መሓ4፥1፤ ኢሳ33፥9፤ሚክ3፥12
22፥7 2ዜና36፥19፤ መዝ74፥5፤ኢሳ10፥34 ፤ኤር4፥7፤6፥4፤ዘካ 11፥1
22፥8 ዘዳ29፥25-26 ፤1ነገ9፥8-9፤ኤር 16፥10-11
22፥9 1ነገ9፥9፤ኤር 16፥11፤ሕዝ39፥23
22፥10 ቍ18:27፤ መክ4፥2፤ኤር24፥9፤ 29፥18፤42፥18፤ሕዝ 24፥16
22፥11 2ነገ23፥31
22፥12 2ነገ23፥34
22፥13 ዘሌ19፥13፤ ኢሳ5፥8፤ሚክ3፥10፤ ፤ዕን2፥9፤ያዕ5፥4
22፥14 2ሳሙ 7፥2፤ኢሳ5፥8-9፤ሕዝ 23፥14
22፥15 2ነገ23፥25፤ መዝ128፥2፤ኢሳ3፥10
22፥16 መዝ36፥10 ፤72፥1-4:12-13፤ 82፥3፤ምሳ24፥23
22፥17 ዘዳ28፥33፤ 2ነገ24፥4፤ኢሳ56፥11 ፤ሕዝ18፥12፤ሚክ2፥2

[T]11 *ኢዮአካዝ ተብሎም ይጠራል*

አል (27፥17 *ይመ*)::

22፥6 *ገለዓድ ... ሊባኖስ፤* እነዚህ ተራሮች በሸፈናቸው ጫካ የታወቁ ነበሩ፤ በተለይ ከሊባኖስ ጫካ ለቤተ *መንግሥት መሥሪያ የሚሆን* ዝግባ ይገኝ ነበር (የ21፥14 ማብ ይመ፤ በተጨ*ማሪም* 1ነገ5፥6:8-10፤ 7፥2-3፤ 10፥27 *ይመ*)::

22፥7 *አዘጋጃለሁ፤* ለዚህ የገባው የዕብራይስጡ ቃል በቀሙ ሲተረጐም፣ "እቀድሳለሁ" የሚል ይሆናል (የ6፥4 *ማብ ይመ*):: *አጥፊዎችን፤* ባቢሎናውያንን ማለት ነው (የ4፥7 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 12፥12 *ይመ*):: *በነፍስ ወከፍ መሣሪያ የሚይዙትን፤* ሕዝ9፥2 *ይመ*:: *የዝግባ ዛፎችን ይቈርጣሉ፤* ከኢሳ 10፥33-34 ጋር ያነጻጽሩ፤ በተለይ የባቢሎናውያን ሰራዊት የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅደስ ደጆች በመጥረቢያና በመዶሻ ስለ መሰበራቸው ጕልሕ አድርጎ የሚገልጸውን ክፍል ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (*መዝ*74፥3-6)::

*22፥8-9፤* የዚህ ክፍል ሐሳብ በ1ነገ 9፥8-9 ላይ ተንጸባርቆ አል፤ ዘዳ29፥24-26 *ይመ*::

22፥9 *ኪዳን ትተው ሌሎችን አማልክት ... ስላገለገሉ፤* በሙሴ ሕግ ውስጥ የተጠቀሱትን አንደኛውንና ሁለተኛውን ትእዛዛት ፈጽሞ መጣስ ነው (ዘፀ20፥3-5 እና ማብ *ይመ*)::

22፥10 *ለሞተው አታልቅሱ፤* ለኢዮስያስ ነው፤ ኢዮስያስ የተለቀሰለት ከሞተ ከብዙ ጊዜ በኋላ ነበር (2ዜና 35፥24-25 *ይመ*):: *ለተማረከው፤* ኢዮአክስ/ ሰሎም ነው:: በ609 ዓ.ቅ.ክ ፈር*ዖን* ኒካዑ "ወደ ግብፅ ይዞት ሄደ፤ በዚያም ሞተ" (2ነገ23፥34)::

22፥11 *ሰሎ፤* የኢዮስያስ አራተኛ ወንድ ልጅ ነበር (1ዜና3፥15 *ይመ*):: "ሰሎም" የቀድሞ መጠሪያ ስሙ ሲሆን፣ "ኢዮአክስ" የሚለው ግን የንግሥ ስሙ ነበር (የንግሥ ስሙ ትርጕም፣ "እግዚአብሔር ይይዛል" ማለት ነው)::

22፥12 *ተማርኮ በሄደበት አገር፤* ግብፅን ያመለክታል (የቍ10 ማብ *ይመ*)::

*22፥13-19፤* በንጉሥ ኢዮአቄም ላይ የተሰነዘረ ጽኑ ዘለፋ ነው፤ አገላለጡም እንደ ሦስተኛ ሰው (ቍ13-14)፣ ከዚያም በኋላ በሽሙጥ እንደ ሁለተኛ መደብ (ቍ15:17)፣ በመጨረሻም ስሙ ተጠቅሶአል (ቍ18)፤ የስሙም ትርጕም፣ "እግዚአብሔር አን*ሥቶ ያቆማል*" ማለት ነው:: ደጉ ንጉሥ ኢዮስያስ በቍ15-16 ላይ በንጽጽር መልክ ቀርቦ ተጠቅሶአል::

22፥13 ... *ለሚሠራ (ወዮለት)፤* ዕን2፥9:12 *ይመ*:: *በግፍ ... ፍትሕ በማዛባት፤* ከቍ3፤ 21፥12 ጋር ያገናዝቡ:: *ሰገነቱንም፤* የመሳ3፥20 ማብ *ይመ*:: *ወገኑን በነጻ ለሚያሠራ፤* ሕጉ ከሚያዘው ውጭ ማለት ነው (ዘሌ25፥39፤ዘዳ24፥14-15 *ይመ*):: ኢዮአቄም ያልከፈላቸው በዐቅም ማነስ ሊሆን ይችላል፤ ምክንያቱም በእርሱ ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ ግብፅ በይሁዳ ላይ ከባድ የግብር ጫና ጥላባት ነበር (2ነገ23፥35 *ይመ*)::

22፥14 *ሰፋፊ መስኮቶችን፤* እነዚህ መስኮቶች ምናልባት እ.ኤ.አ በ1960 ዓ.ም የሥነ ቅርስ ተመራማሪዎች በቤትሐካሪም በቍፋሮ ካገኟቸው መስኮቶች ጋር ተመሳሳይ ሳይሆኑ አይቀሩም (6፥1፤ የነህ3፥14 ማብ *ይመ*):: *ያስጌጠዋል፤* የበሮችንና የመስኮቶችን ጠርዝ ማስጌጥ ከአንዳንድ ሁኔታዎች አኳያ ሲታይ የቅንጦት ነገር በመሆኑ፣ ነቢዩ ሐጌ ነቅፎታል (ሐጌ1፥4)::

22፥15 *አባትህስ፤* ኢዮስያስ ነው:: *የሚበላውና የሚጠጣው ... ነበርን?* ተድላ ደስታ ነበረው ማለት ነው (መክ2፥24-25፤ 3፥12-13 *ይመ*):: *ፍትሕንና ጽድቅን በማድረጉ፤* እንደ አባቱ እንደ ዳዊት ማለት ነው (2ሳሙ8፥15 *ይመ*)፤ ከቍ13 ጋር ያገናዝቡ (የዚህኑ ቍ ማብ *ይመ*)::

*22፥16፤* ሐዋርያው ያዕቆብም ከእግዚአብሔር ጋር ሊኖረን የሚገባው ትክክለኛው ግንኙነት ምን እንደ ሆነ፣ በተመሳሳይ መልክ ይገልጻል (ያዕ1፥27 *ይመ*)፤ ከ5፥28 ጋር ያገናዝቡ (የዚያኑ ቍ ማብ *ይመ*):: *የድኾችንና የችግረኞችን፤* የ20፥13 ማብ *ይመ*:: *እኔን ማወቅ፤* እግዚአብሔርን በሙሉ ልብ መውደድ ማለት ነው፤ ይህም በጥልቅ መንፈሳዊ ሕይወት ለመራመድና የተቸገሩትን ለመርዳት ያነሣሣል (ዘዳ10፥12-13፤ ሆሴ6፥6፤ ሚክ 6፥8 *ይመ*)::

22፥17 *የአንተ፤* የኢዮአቄም ማለት ነው (ቍ18 *ይመ*):: *አጭበርብሮ ጥቅምን በማግኘት፤* 6፥13፤8፥10 *ይመ*:: *የንጹሑን ደም በማፍሰስ፤* የ19፥4 ማብ ይመ፤ በዚህ ረገድ የኢዮአቄም ጭካኔ ምን ያህል እንደ ነበር በ26፥20-23 ላይ *ይመ*:: *ጭቈናንና፤* ቍ3፤ 6፥6፤ 21፥12 *ይመ*::

18ስለዚህ *እግዚአብሔር* ስለ ይሁዳ ንጉሥ ስለ ኢዮስያስ ልጅ ስለ ኢዮአቄም እንዲህ ይላል፤

"'ዋይ ወንድሜ! ዋይ፣ እኅቴን!'
ብለው አያለቅሱለትም።
'ዋይ፣ ጌታዬን! ዋይ፣ ለግርማዊነቱ!'
ብለውም አያለቅሱለትም።
19አህያ እንደሚቀበር ይቀበራል፤
ከኢየሩሳሌም በሮች ውጪ፤
ተጐትቶ ይጣላል።

20"ሊባኖስ ላይ ወጥተሽ ጩኺ፤
ድምፅሽን በባሳን አሰሚ፤
በዓባሪም ሆነሽ ጩኺ፤
ወዳጆችሽ ሁሉ ወድመዋልና።
21ተመችቶሽ በነበረ ጊዜ አስጠነቀቅሁሽ፤
አንቺ ግን፣ 'አልሰማም' አልሽ፤
ከትንሽነትሽ ጀምሮ መንገድሽ ይኸው ነበር፤
ቃሌንም አልሰማሽም።
22እረኞችሽ ሁሉ በነፋስ ይወሰዳሉ፤
ወዳጆችሽም ተማርከው ይሄዳሉ፤
ከክፋትሽም ሁሉ የተነሣ፣
ታፍሪያለሽ፤ ትዋረጃለሽም።
23አንቺ፣ 'በሊባኖስ'[ሀ] ውስጥ የምትኖሪ፣
መኖሪያሽን በዝግባ ዛፍ የሠራሽ ሆይ፤
ምጥ እንደ ያዛት ሴት፣
መከራ በላይሽ ሲመጣ ጩኸትሽ
እንዴት ይሆን!

24"በሕያውነቴ እምላለሁ"፤ ይላል *እግዚአብሔር* "የይሁዳ ንጉሥ የኢዮአቄም ልጅ ኢኮንያን[ለ] የቀኝ እጄ የቀለበት ማኅተም ብትሆን እንኳ ኖሮ፣ አውልቄ እጥልሃለሁ"፤ 25"ሕይወትህን ለሚሿት፣ ለምትፈራቸው ለባቢሎናውያንና[ሐ] ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደነፆር አሳልፌ እሰጥሃለሁ። 26አንተንና የወለደችህን እናትህን ወዳልተወለዳችሁበት ወደ ሌላ አገር ወርውሬ እጥላችኋለሁ፤ በዚያም ትሞታላችሁ። 27ልትመለሱባት ወደምትናፍቋት ምድር ከቶ አትመለሱም።"

28ይህ ኢኮንያን የተባለ ሰው፣ የተናቀና
የተሰበረ ገምቦ፣
ማንም የማይፈልገው ዕቃ ነውን?
እርሱና ልጆቹ ለምን ወደ ውጪ ተጣሉ?
ወደማያውቁትስ ምድር ለምን
ተወረወሩ?
29ምድር ሆይ፤ አንቺ ምድር፣ አንቺ
ምድር፤
የእግዚአብሔርን ቃል ስሚ!
30*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"አንድ እንኳ የረባ ዘር የማይወጣለት፣

22፥18 2ሳሙ1፥26
22፥19 2ነገ24፥6፤ ኤር8፥2፤36፥30
22፥20 ቍ22፤ዘኍ 27፥12፤መዝ68፥15፤ ኢሳ57፥13፤ኤር30፥ 14፤ሰቆ1፥19፤ሕዝ 16፥33-34፤ሆሴ8፥9
22፥21 ዘዳ9፥7፤ መዝ25፥7፤ኢሳ54፥4፤ ኤር3፥13፤25፤7፥23-28፤31፥19፤32፥30፤ ሶፎ3፥2፤ዘካ 7፥7
22፥22 ቍ20፤ዘዳ 28፥64፤ኢዮ27፥21፤ ኤር7፥19፤10፥21
22፥23 1ነገ 7፥2፤ ኤር4፥31፤ሕዝ17፥3
22፥24 ዘፍ38፥18፤ 2ነገ24፥6፡8
22፥25 2ነገ24፥16፤ 2ዜና36፥10
22፥26 1ሳሙ25፥ 29፤ 1ነገ2፥19፤ 2ነገ24፥8፤2ዜና 36፥10፤ኢሳ22፥17፤ ሕዝ19፥9-14
22፥27 ቍ 10
22፥28 2ነገ24፥6፤ መዝ31፥12፤ኤር15፥1 ፤17፥4፤19፥10፤ 25፥34፤48፥38
22፥29 ኤር6፥19
22፥30 1ዜና3፥18፤ ኢዮ18፥19፤መዝ 94፥20፤ኤር10፥21፤ 38፥23፤52፥10፤ማቴ 1፥12

[ሀ]23 *ሊባኖስ* የተባለው በኢየሩሳሌም ያለው ቤተመንግሥት ነው (1ነገ7፥23 ይመ)
[ለ]24 በዕብራይስጥ *ኮንያ* ሲሆን *የኢዮአኪን* አቻ ስም ቃል ነው፤ ቍ28 ይመ።
[ሐ]25 ወይም *ከለዳውያን*

*22፥18፤* ከ2ዜና35፥24-25 ጋር ያገናዝቡ። *"ዋይ፣ ወንድሜ! ..." ብለው አያለቅሱለትም፤* ከ1ነገ13፥30 ጋር ያገናዝቡ።

22፥19 *አህያ እንደሚቀበር ይቀበራል፤* ጨርሶ አይቀበርም እንደ ማለት ነው (36፥30 ይመ)፤ የተፈጸመው በ2ነገ24፥6 ላይ ነው፤ በዚያ ቦታ ላይ ስለ ቀብሩ የተነሣ ነገር የለም፤ ነገር ግን ኢዮአቄም "ከአባቶቹ ጋር ዐረፈ" ይህ ደግሞ ለዘብ ባለ አገላለጽ "ሞተ" ማለት ነው (የዘፍ 25፥8፤ የ1ነገ 1፥21 ማብ ይመ)። *ተጐትቶ ይጣላል፤* 15፥3 ይመ።

*22፥20-23፤* እግዚአብሔር በሴት *የታ* በሰውኛ ዘይቤ ለተገለጠችው (ቍ23 ይመ) ለኢየሩሳሌም በዚህ ክፍል ሲናገራት ይታያል።

22፥20 *ሊባኖስ ... በባሳን ... በዓባሪም፤* ተራራማ ቦታዎች ናቸው (ቍ6፤ ዘኍ 27፥12፤ 33፥47-48፤ ዘዳ 32፥49፤ መሳ 3፥3፤ መዝ68፥15 ይመ)፤ የመጀመሪያዎቹ ሁለቱ በሰሜን፣ ሦስተኛውም በደቡብ በኩል የሚገኙ ሲሆኑ፣ መልስ አዘል በሆነ አቀራረብ፣ መላ የእስራኤልን ምድር ለማመልከት የሚያስችሉ ከፍታዎች ናቸው። ወዳጆችሽ፤ የተባበረቻቸውን ፍቅረኞች የሚያመለክት ነው (4፥30 እና ማብ ይመ)፤ ቃሉ እዚህ ላይ በስምምነት ግንባር የፈጠሩ ወገኖችን ያመለክታል። አንድ ጊዜ የይሁዳ ግብረ አበር ከነበሩት ውስጥ ግብፅ፣ አሦር (2፥36 ይመ)፣ ኤዶም፣ ሞዓብ፣ አሞንና፣ ፊንቄ ይገኛሉ (27፥3 ይመ)፤ እነዚህም ሁሉ በባቢሎን ድል ተመትተዋል ወይም ድል ሊመቱ ጥቂት ጊዜ ይቀራቸው ነበር (27፥6-7፤ 28፥14 ይመ)። *ወድመዋልና፤* 14፥17 ይመ።

22፥21 *'አልሰማም' አልሽ ... ቃሌንም አልሰማሽም፤* 7፥22-26፤ 11፥7-8 ይመ። *ከትንሽነትሽ፤* በግብፅ አገር በነበሩበት፣ በጥንቱ የእስራኤል ታሪክ ዘመን (2፥2 እና ማብ፤ ሆሴ 2፥15 ይመ)።

22፥22 *እረኞችሽ ... ይወሰዳሉ፤ ... ከክፋትሽም፤* በዕብራይስጡ የመጀመሪያዎቹ ሁለት ቃላት ሥርወ ቃል አንድ ነው፤ የሦስተኛውም በጣም ተቀራራቢ ነው። "እረኞች" ለሚለው 2፥8 እና ማብ፤ 10፥21፤ 23፥1-4 ይመ። ይህ ጥቅስ በመጀመሪያ ደረጃ ተፈጻሚነት ያገኘው በ597 ዓ.ቅ.ክ ነበር (2ነገ24፥12-16 ይመ)። *በነፋስ ይወሰዳሉ፤* 13፥24፤ ኢዮ27፥21፤ ኢሳ27፥8 ይመ።

22፥23 *በሊባኖስ ... በዝግባ፤* 'ሊባኖስ' የሚለው ቃል ከሊባኖስ በመጣ ዝግባ የተሠራውን፣ በኢየሩሳሌም የሚገኘውን ቤተ መንግሥት ያመለክታል፤ በተጨማሪም 21፥14 እና ማብ፤ ሕዝ 17፥3-4፡12 ይመ። *ምጥ እንደ ያዛት ሴት ... መከራ፤* 4፥31፤ 6፥24፤ 13፥21 ይመ፤ በተጨማሪም የ4፥19 ማብ ይመ።

*22፥24-30፤* በንጉሥ ኢኮንያን ላይ የተነገረ ትንቢት ነው (በ24፥1፤ 29፥2 ላይ ተፈጽሞአል)። የንጉሡ የስም ትርጒም፣ "እግዚአብሔር ይመሠርታል" ማለት ሲሆን፣ አንዳንድ ጊዜ "ኢዮአኪን" ተብሎ ይጠራል።

22፥24 *በሕያውነቴ እምላለሁ፤* የዘፍ42፥15 ማብ ይመ። *የ... እጄ የቀለበት ማኅተም ብትሆን እንኳ ኖሮ፤* በኢዮኪን ላይ የተወሰነው ፍርድ በሐጌ 2፥23 ላይ የታጠፈ ይመስላል (የዚያው ማብ ይመ)።

22፥25 *ለምትፈራቸው ... አሳልፌ እሰጥሃለሁ፤* ከ39፥17 ጋር ያገናዝቡ።

*22፥26፤* በዚህ ቍጥር ላይ የተነገረው በ597 ዓ.ቅ.ክ ተፈጽሞአል (29፥2፤ 2ነገ24፥15 ይመ)። *አንተንና የወለደችህን እናትህን፤* ኢኮንያንንና ኔስታንን ነው (የ13፥8 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 2ነገ24፥8 ይመ)። *ወደ ሌላ አገር ወርውሬ እጥላችኋለሁ፤* በምርኮ ወደ ባቢሎን ምድር እሰድዳችኋለሁ ማለት ነው (7፥15፤ 16፥3፤ ዘዳ29፥18 ይመ)።

*22፥28፤* መልስ አዘል ጥያቄ ነው፤ መልሱም በቍ30 ላይ በግልጽ ተቀምጦአል። *የተሰበረ ገምቦ ... ወደ ውጭ ተጣሉ፤* ኢዮአኪንና ከእርሱ የተገኘው ዘር፣ ልክ እንደ ይሁዳ (19፥10-11 ይመ) በእግዚአብሔር ፍርድ ሥር ናቸው። *እርሱና ልጆቹ፤* ኢዮአኪን በምርኮ በተወሰደ ጊዜ ገና የ18 ዓመት ወጣት ነበር (2ነገ24፥8 ይመ)፤ ይሁን እንጂ በዚህ ጊዜ ከአንድ በላይ አግብቶ ነበር (2ነገ24፥15 ይመ)፤ ስለዚህ አንድ ወይም ከዚያ በላይ ልጆች ሊኖሩት ይችላል።

22፥29 *ምድር ሆይ፤ አንቺ ምድር፣ አንቺ ምድር፤* የቃሉ መደጋገም የነገሩን ክብደትና የተሰጠውን አጽንዖት ያሳያል (7፥4፤ 23፥30-32፤ ሕዝ 21፥27 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ6፥3 ማብ ይመ)።

22፥30 *መካን፤* ኢዮአኪን ጨርሶ ልጅ የሚባል አልነበረውም ለማለት ሳይሆን (ቢያንስ ሰባት ልጆች ነበሩትና፤ 1ዜና3፥17-18 ይመ)፣ በይሁዳ ምድር በዳዊት ዙፋን ላይ

አንድ እንኳ በዳዊት ዙፋን የሚቀመጥ፣
ወይም በይሁዳ የሚገዛ የማይኖረው
ነውና፤
በሕይወት ዘመኑ የማይከናወንለት፣
መካን ሰው ብላችሁ መዝግቡት።።"

## ጻድቁ ቅርንጫፍ

**23** "በማሰማሪያ ቦታዬ ያሉትን በጎቼን ለሚያጠፉና ለሚበትኑ እረኞች ወዮ ላቸው!" ይላል *እግዚአብሔር።* [2]ስለ ዚህ የእስራኤል ስምላክ *እግዚአብሔር* ሕዝ ቤን ስለሚጠብቁ እረኞች እንዲህ ይላል፤ "መንጋዬን ስለ በተናችሁ፣ ስላባረራችሁና ተገቢውን ጥንቃቄ ስላላደረጋችሁላቸው፣ ለክፉታችሁ ተገቢውን ቅጣት አመጣባቸ ኋለሁ" ይላል *እግዚአብሔር፤* [3]"የመንጋዬ ንም ቅሬታ ካባረርሁባቸው አገሮች ሁሉ እኔ ራሴ ሰብስቤ፣ ወደ መሰማሪያቸው እመ ልሳቸዋለሁ፤ በዚያም ፍሬያማ ይሆናሉ፤ ይበ ዛሉም። [4]የሚጠብቋቸውን እረኞች አስነሣ ላቸዋለሁ፤ ከእንግዲህም አይፈሩም፤ አይደ ነግጡም ከእነርሱም አንድ እንኳ አይጐድ ልም" ይላል *እግዚአብሔር።*

[5]"እነሆ፤ ለዳዊት፣[ም]
ጻድቅ ቅርንጫፍ የማስነሣበት ጊዜ
ይመጣል፤
እርሱም ፍትሕንና ጽድቅን የሚያደርግ፣
በጥበብ የሚገዛ ንጉሥ ይሆናል" ይላል
*እግዚአብሔር።*
[6]በእርሱም ዘመን ይሁዳ ይድናል፤
እስራኤልም በሰላም ይኖራል፤
የሚጠራበትም ስም፣
'*እግዚአብሔር ጽድቃችን*' የሚል ነው።

[7]"ስለዚህ ሰዎች፣ 'እስራኤላውያንን ከግ ብፅ ምድር ያወጣ ሕያው *እግዚአብሔርን*' ብለው ከእንግዲህ የማይምሉበት ዘመን ይመጣል" ይላል *እግዚአብሔር፤* [8]ነገር ግን፣ 'እስራኤልን ከሰሜን ምድርና እነርሱን ከበተነባቸው ከሌሎች አገሮች ያወጣ ሕያው *እግዚአብሔርን*' ይላሉ፤ ከዚያ በኋላ በገዛ ምድራቸው ይኖራሉ።

## ሐሰተኛ ነቢያት

[9]ስለ ነቢያት፣
ልቤ በውስጤ ተሰብሮአል፤
ዐጥንቶቼም ተብረክርከዋል፤
*ከእግዚአብሔር* የተነሣ፣
ከቅዱስ ቃሉም የተነሣ፣
የወይን ጠጅ እንዳሸነፈው፣
እንደ ሰካራም ሰው ሆኛለሁ።
[10]ምድሪቱ በአመንዝሮች ተሞልታለች፤
ከርግማን የተነሣ[ሣ] ምድሪቱ ታለቅሳለች፤
በምድረ በዳ ያሉት መሰማሪያዎች
ደርቀዋል።[ሬ]

ም5 ወይም *ከዳዊት የዘር ግንድ*
ሣ10 ወይም *ከእነዚህ ነገሮች የተነሣ*
ሬ10 ወይም *ምድሪቱ ደርቃለች*

23፥1 መዝ100፥3፤ ኢሳ56፥11፤ኤር10፥21፤12፥10፤13፥17፤25፥36፤ሕዝ34፥1-10፡31፤ዘካ10፥2፤11፥15-17፤
23፥2 ኤር10፥21፤13፥20፤21፥12፤ሕዝ34፥8-10፤ዮሐ10፥8
23፥3 1ነገ8፥48፤ኢሳ11፥10-12፤ኤር32፥37፤ሕዝ34፥11-16
23፥4 ዘፍ48፥15፤ ኢሳ31፥4፤ኤር31፥10፤30፥10፤46፥27-28፤ ዮሐ6፥39
23፥5 ዘፍ18፥19፤ 2ነገ19፥26፤ኢሳ4፥2፤9፥7፤ሕዝ17፥22፤ማቴ1፥1፤2፥2
23፥6 ዘዐ23፥21፤ ዘሌ25፥18፤ዘዳ32፥8፤ዕዝ9፥15፤ኢሳ42፥6፤ ኤር33፥16፤ሆሴ2፥18፤ ማቴ1፥21-23፤ሮሜ3፥21-22፤1ቆሮ1፥30
23፥7 ዘዳ15፥15፤ ኤር30፥3
23፥8 ኢሳ14፥1፤ 43፥5-6፤ኤር30፥10፤ሕዝ20፥42፤34፥13፤ አሞ9፥14-15
23፥9 ኢዮ4፥14፤ ኤር4፥19፤20፥8-9
23፥10 ዘዳ28፥23-24፤መዝ107፥34፤ኤር4፥26፤9፥2፡10፤12፥11

የሚቀመጥ አንድም ልጅ እንደማይኖረው ለመግለጽ ነው። የኢዮአኪን (የኢኮንያን) የልጅ ልጅ ዘሩባቤል (1ዜና3፥17-19፤ ማቴ1፥12 ይመ) የይሁዳ ገዥ ሆኖአል (ሐጌ1፥1 ይመ)፤ ንጉሥ ግን አልሆነም። ሴዴቅያስ የኢዮስያስ ልጅ ነበረ (37፥1 ይመ)፤ የኢኮንያን (የኢዮአኪን) ልጅ አልነበረም፤ እርሱና ልጆቹም የሞ ቱት ከኢኮንያን በፊት ነበር (52፥10-11 ይመ)፤ ስለዚህ ኢዮአ ኪን (ኢኮንያን) እስከ ክርስቶስ ድረስ ከነበረው የዳዊት ሥርወ መንግሥት የመጨረሻው የይሁዳ ንጉሥ ነበር።

*23፥1-8፤* እግዚአብሔር የይሁዳን ክፉ ገዦችና መሪዎች ለመቅጣት (ቍ1-2)፣ ሕዝቡንም የኋላ ኋላ ከምርኮ ለመመለስ (ቍ3-4፡7-8) እንዲሁም በመጨረሻ ፍጹም የሆነውን ንጉሥ ከዳ ዊት ቤት ለማስነሣት ማቀዱን የሚያሳይ በአጭሩ የቀረበ ክፍል ነው (የተነገረው በሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት ይሆናል የቍ6 ማብ ይመ)።

*23፥1፤* 10፥21 እና ማብ ይመ። *በጎቼን፤* የይሁዳን ሕዝብ ነው (ቍ2 ይመ)።

23፥2 *ተገቢውን ጥንቃቄ ... ተገቢውን ቅጣት፤* በዕብራ ይስጥ ሁለቱም ሐረጎች ከአንድ ሥርወ ቃል የመጡ ናቸው (ቍ4 እና ማብ ይመ)። የይሁዳ ገዦች ሳይፈጽሙት የቀረ ነገር በሕዝ34፥4 ላይ በአጭሩ ሰፍሮአል።

23፥3 *ቅሬታ፤* የ6፥9፤ የኢሳ10፥20-22 ማብ ይመ። *ካባረርሁባቸው፤* የይሁዳ ኀጢአትና የመሪዎቻቸው በደል ከአገር "ቢያባርራቸውም" (ቍ2)፣ ሕዝቡ የገባውን ኪዳን ደጋግሞ በማ ፍረስ ያስከተለውን መዘዝ በመጨረሻ ላይ ጌታ ራሱ ከግቡ አድርሶታል። *ፍሬያማ ይሆናሉ፤ ይበዛሉም፤* የዘፍ1፥28 ማብ ይመ።

23፥4 *አይፈሩም፤ አይደነግጡም፤* ለመንጋው የሚያስብ እረኛ ከሌለ፣ አጥቂ አውሬ እንደሚያሠጋቸው ያመለክታል (ሕዝ 34፥8 ይመ)። *አይጐድልም፤* ዘኍ31፥49 ይመ። ለዚህ ቃል የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል "ተገቢውን ጥንቃቄ"፣ "ተገቢ ውን ቅጣት" ለሚሉት ሐረጎች ከገባው ጋር ከተመሳሳይ ሥርወ ቃል የመጣ ነው (ቍ2 እና ማብ ይመ)።

*23፥5-6፤* በኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ ስለ መሲሑ ከሚና ገሩት ዋና ዋና ክፍሎች አንዱ ነው፤ እንደ ገናም በ33፥15-16 ላይ ተገልጦ ይታያል።

23፥5 *የማስነሣበት፤* 2ሳሙ7፥12 ይመ፤ በተጨማሪም 30፥9፤ ሕዝ34፥23-24፤ 37፥24 ይመ። *ለዳዊት፤* "ከዳዊት ቤት" ተብሎ ሊተረጐምም ይችላል፤ በተጨማሪም ማቴ1፥1 ይመ። መሲሑ ከዚህ ቀደም ከዳዊት ቤት ተነሥተው ከነገሡት ነገሥታት ሁሉ የተለየ ፍጹም ንጉሥ ነው፤ ባሕርዩ የምርጥ ገዦችን የላቀ በጎነት አሟልቶ የሚይዝና ከዚያም በላይ ማንም ሊደርስበት የማይችል ባሕርይ አለው። *ቅርንጫፍ፤* ለመሲሑ የተሰጠ መጠሪያ ነው (የኢሳ4፥2 ማብ ይመ)። 'ታርጉም' የተባ ለው የጥንቱ የአራማይክ የቅዱሳት መጻሕፍት ፍቺ እዚህ ቦታ ላይ "መሲሕ" የሚለውን ቃል አስገብቶአል። *በጥበብ የሚገዛ፤* የኢሳ52፥13 ማብ ይመ። *ፍትሕና ጽድቅን የሚያደርግ፤* 22፥3፡ 15 ይመ፤ ለንጉሥ ዳዊትም እንደዚሁ ተነግሮለታል (2ሳሙ 8፥15 ይመ)።

23፥6 *ይሁዳ ... እስራኤልም፤* ዳግም የተባበረው የእግዚ አብሔር ሕዝብ በምድሩ ላይ ተመልሶ ይተከላል (ሕዝ37፥15-22 ይመ)። *ይድናል ... በሰላም ይኖራል፤* ትድግናው መንፈሳዊም፣ አካላዊም ይሆናል (ዘዳ33፥28-29 ይመ)። *እግዚአብሔር ጽድቃ ችን፤* ከዚህ በላይ እንደ ተመለከተው ሴዴቅያስ እንደ ስሙ ትርጕም መኖር ባይችልም፣ "እግዚአብሔር ጽድቁ ነው" የተባ ለው መሲሑ ኢየሱስ በሕዝቡ ላይ የተትረፈረፈ በረከት ያወር ዳል (ሕዝ34፥25-31 ይመ)፤ ይህም በረከት የሚመጣው "ፍትሕ ንና ጽድቅን ከሚያደርገው" (ቍ5) ታላቅ ንጉሥ እጅ ነው።

*23፥7-8፤* አብዛኛው ከ16፥14-15 ቃል በቃል የተጠቀሰ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)።

*23፥9-40፤* ሐሰተኞች ነቢያት የተወገዙበት ክፍል ነው (2፥8፤4፥9፤5፥30-31፤6፥13-15፤ 8፥10-12፤14፥13-15፤ 18፥18-23፤ 26፥8፡11፡16፤27-28፤ኢሳ28፥7-13፤ሕዝ13፤ሚክ3፥5-12 ይመ)።

23፥9 *ስለ፤* ርእሶችን የሚያስተዋውቅ ቃል ሆኖ በ46፥2፤ 48፥1፤ 49፥1፡7፡23፡28 ላይም ጥቅም ላይ ውሎአል። *ከቅዱስ ቃሉም፤* የሐሰተኛ ነቢያት ቃል ከዚህ ጋር ያገናዝቡ (ቍ16-18 ይመ)።

*23፥10፤* ኢሳ24፥4-6 ይመ። *በአመንዝሮች፤* 5፥7-8፤ 9፥2 ይመ፤ በተጨማሪም 2፥20 ማብ ይመ። *ከርግማን፤* የእግዚ አብሔርን ኪዳን በማፍረስ የሚደርስ ነው (11፥3 እና ማብ፤ 11፥8 ይመ)። *ታለቅሳለች ... ደርቀዋል፤* 12፥4 እና ማብ ይመ።

ነቢያቱም ጠማማ መንገድ ተከትለዋል፤
ሥልጣናቸውን ያለ አግባብ
ተጠቅመዋል።

[11]“ነቢዩም፣ ካህኑም በጽድቅ መንገድ
የማይሄዱ ናቸው፤
በቤተ መቅደሴ እንኳ ሳይቀር
ክፋታቸውን አይቻለሁ።”
ይላል እግዚአብሔር።
[12]“ስለዚህ መንገዳቸው ድጥ ይሆናል፤
ወደ ጨለማ ይጣላሉ፤
ተፍገምግመውም ይወድቃሉ፤
በሚቀጡበትም ዓመት፣
መዓት አመጣባቸዋለሁ፤”
ይላል እግዚአብሔር።
[13]“በሰማርያ ባሉ ነቢያት ላይ፣
ደስ የማያሰኝ ነገር አይቻለሁ፤
በበኣል ስም ትንቢት ተናገሩ፤
ሕዝቤን እስራኤልን አሳቱ።
[14]በኢየሩሳሌም ባሉ ነቢያትም ላይ፣
የሚዘገንን ነገር አይቻለሁ፤
ያመነዝራሉ፤ በመዋሸትም ይኖራሉ፤
ማንም ከክፋቱ እንዳይመለስ፣
የክፉዎችን እጅ ያበረታሉ፤
በእኔ ዘንድ ሁሉም እንደ ሰዶም፣
ነዋሪዎቿም እንደ ገሞራ ናቸው።”

[15]ስለዚህ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ስለ እነዚህ ነቢያት እንዲህ ይላል፤

“ከኢየሩሳሌም ነቢያት፣
በምድሪቱ ሁሉ ርኵሰት ተሠራ
ጭቶአልና፤
መራራ ምግብ አበላቸዋለሁ፤
የተመረዘም ውሃ አጠጣቸዋለሁ።”

[16]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

“እነዚህ ነቢያት የሚተነብዩላችሁን
አትስሙ፤
በባዶ ተስፋ ይሞሏችኋል፤
ከእግዚአብሔር አፍ የወጣ ሳይሆን፣
ከገዛ ልባቸው የሆነውን ራእይ
ይናገራሉ።
[17]እኔን ለሚንቁኝ፣
‘እግዚአብሔር ሰላም ይሆንላችኋል
ብሏል’ ይላሉ፤
የልባቸውን እልኸኝነት ለሚከተሉም ሁሉ፣
‘ክፉ ነገር አይነካችሁም’ ይሏቸዋል።
[18]ቃሉን ለማየትና ለመስማት፣
እነማን የእግዚአብሔር ምክር ባለበት
ቆመዋል?
ቃሉን ያደመጠ፣ የሰማስ ማን ነው?
[19]እነሆ፤ የእግዚአብሔር ዐውሎ ነፋስ፣
በቍጣ ይነሣል፤
ብርቱም ማዕበል፣
የክፉዎችን ራስ ይመታል።
[20]እግዚአብሔር የልቡን ሐሳብ፣
ሙሉ በሙሉ ሳይፈጽም፣
ቍጣው እንዲሁ አይመለስም፤
በኋለኛው ዘመን፣
ይህን በግልጽ ትረዳላችሁ።
[21]እኔ እነዚህን ነቢያት አልላክኋቸውም፤
እነርሱ ግን ለራሳቸው መልእክታቸውን
ይዘው ሮጡ፣
ሳልናገራቸውም፣
ትንቢት ተናገሩ።
[22]ምክሬ ባለበት ቢቆሙ ኖሮ፣
ቃሌን ለሕዝቤ ባሰሙ ነበር፤
ከክፉ መንገዳቸው፣
ከክፉ ሥራቸውም በመለሷቸው ነበር።

[23]“እኔ የቅርብ ስምባክ ብቻ ነኝን?
ይላል እግዚአብሔር፤
“የሩቅስ ስምባክ አይደለሁምን?

23፥11 2ነገ21፥4፤ ኤር6፥13፤7፥10፤ 8፥10፤ሶፎ3፥4
23፥12 ዘዳ32፥35፤ ኢዮ3፥23፤ኤር11፥23 ፤13፥16
23፥13 ቍ32፤1ነገ 18፥22፤ኢሳ3፥12፤ ሕዝ13፥10
23፥14 ቍ22፤ ዘፍ18፥20፤ኢሳ5፥18፤ ኤር5፥30፤ 0፥16፤ 29፥23፤ሆሴ6፥10፤ አሞ4፥11፤ማቴ11፥24
23፥15 ኤር8፥10፡ 14፤9፥15
23፥16 ኤር9፥20፤ 14፥14፤27፥9-10፡14 ፤ሕዝ13፥3፤ማቴ7፥15
23፥17 ቍ31፤1ነገ 22፥8፤ኤር4፥10፤5፥ 12፤13፥10፤አሞ9፥10 ፤ሚክ3፥11
23፥18 1ነገ22፥19፤ ሮሜ11፥34
23፥19 ኢሳ30፥30፤ ኤር25፥32፤30፥23፤ ዘካ7፥14
23፥20 2ነገ23፥36፤ ኤር4፥28
23፥21 ኤር14፥14፤ 27፥15
23፥22 ቍ14፤ዘዳ 33፥10፤1ነገ22፥19፤ 2ነገ17፥13፤ኤር25፥5 ፤አሞ3፥7፤ዘካ1፥4
23፥23 መዝ139፥1-10

ባዕዳን አማልክትን ማምለክ ምድሪቱ እንዳትለመልም ምክንያት ነው፤ ምክንያቱም ልምላሜን የሚሰጠው እግዚአብሔር ብቻ ነው (ሆሴ2፥5-8:21-22፤ አሞ4፥4-9 ይመ)። *በምድረ በዳ ያሉት መሰማሪያዎች፤* የ9፥10 ማብ ይመ። *ጠማማ መንገድ፤* የእግዚአብሔርን ሳይሆን፣ የራሳቸውን መንገድ ስለሚከተሉ አካሄዳቸው ከመስመር የወጣ ነው (8፥6 ይመ)።

23፥11 *በቤተ መቅደሴ እንኳ ሳይቀር ክፋታቸውን፤* ለምሳሌ:- 32፥34፤2ነገ16፥10-14፤21፥5፤ሕዝ8፥5:10:14:16 ይመ።

23፥12 *መንገዳቸው ድጥ ይሆናል፤ ወደ ጨለማ ይጣላሉ፤* መዝ35፥5-6 ይመ፤ በተጨማሪም መዝ73፥18 ይመ።

23፥13 *በበኣል ስም ትንቢት ተናገሩ፤* 2፥8 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 1ነገ18፥19-40 ይመ።

23፥14 *በመዋሸትም ይኖራሉ፤* 14፥13 ይመ። *እጅ ያበረታሉ፤* የዕብራይስጡ አቻ ሐረግ በሕዝ13፥22 ላይ “አይዞህ ማለት” በሚል ስሜት “ማበረታታት” ተብሎ ተተርጕሞአል። *ማንም ከክፋቱ እንዳይመለስ፤* ሕዝ13፥22 ይመ። *እንደ ሰዶም ... እንደ ገሞራ፤* የ20፥16 ማብ ይመ።

*23፥15፤ ርኵሰት፤* ቍ11 ይመ። ... *የተመረዘም ውሃ አጠጣቸዋለሁ፤* አብዛኛውን በ9፥15 ላይ ካለው ቃል በቃል የተጠቀሰ ነው (የዚያን ቍጥር ማብ ይመ)።

23፥16 *ራእይ፤* “መገለጥ” ወይም “ትንቢት” ማለት ነው (1ሳሙ3፥1፤ ምሳ29፥18፤ ኢሳ1፥1፤ አብ1 ይመ)። *ከገዛ ልባቸው፤* ቍ26፤ 14፥14 ይመ። *ሐሰተኞች ነቢያት “የተለየ ወንጌል” እንደሚያስተምሩት ያሉ ናቸው (ገላ1፥6-9)።*

23፥17 *ሰላም ይሆንላችኋል፤* ሐሰተኞች ነቢያት ብዙውን ጊዜ ለሰዎች የሚያቀርቡት መልእክት ነው (6፥14 እና ማብ፤ 8፥11፤ 14፥13 እና ማብ ይመ፤ ከ28፥8-9 ጋር ያነጻጽሩ)። *የልባቸውን እልኸኝነት፤* የ3፥17 ማብ ይመ።

23፥18 *የእግዚአብሔር ምክር፤* የእግዚአብሔር ባለሟሎች የሚገኙበት በሰማያዊ ስፍራ ያለ ጉባኤ (ቍ22፤ ኢዮ15፥7-10 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 1ነገ22፥19-22፤ ኢዮ1፥6፤ 2፥1፤ 29፥4 እና ማብ፤ መዝ89፥7 ይመ)። በአሞ3፥7 ላይ “ምክር” ለሚለው ቃል የገባው የዕብራይስጡ አቻ ቃል እግዚአብሔር ለተመረጡ አገልጋዮቹ ሊገልጥ ያለውን ዐሳብ ለማመልከት “ዕቅድ” ተብሎ ተተርጕሞአል (ቍ20 ይመ)።

*23፥19-20፤* በ30፥23-24 ላይ ከሞላ ጐደል ቃል በቃል ተደግሞአል።

23፥19 *ዐውሎ ነፋስ ... ብርቱም ማዕበል፤* የእግዚአብሔር ቍጣ ምን እንደሚመስል የሚያመለክት ጕልሕ መግለጫ ነው።

23፥20 *በግልጽ ትረዳላችሁ፤* በ597 ዓ.ቅ.ክ ወደ ባቢሎን ምርኮ ከተወሰዱ በኋላ፣ በዚያ ምድር እንኳ የሚሰሟቸውን ማሳሳት እንዳልተውት ሐሰተኛ ነቢያት አይደለም (29፥20-23 ይመ)።

23፥21 *እኔ ... አልላክኋቸውም፤* ቍ32፤ 29፥9 ይመ፤ ከ1፥7፤ ከኢሳ6፥8፤ ከሕዝ3፥5 ጋር ያገናዝቡ። *ሳልናገራቸውም፤* 29፥23 ይመ።

23፥22 *ምክሬ፤* የቍ18 ማብ ይመ።

23፥23 *የቅርብ አምላክ .... የሩቅስ አምላክ፤* እግዚአብሔር ሰው ሊደርስበት በማይችል ስፍራ ይገኛል፤ በአንጻሩም ከማንም ከምንም የበለጠ በቅርባችን የሚገኝ ነው። በተቀደሰና በከፍተኛ ቦታ ይኖራል፤ ነገር ግን በመንፈሱ ትሑት ከሆነ ሰው ጋርም ዝቅ ብሎ ይናገራል (ኢሳ57፥15 ይመ)።

[24]እኔ እንዳላየው፣
በስውር ቦታ ሊሸሸግ የሚችል አለን?”
ይላል እግዚአብሔር።
“ሰማይንና ምድርንስ የሞላሁ እኔ
አይደለሁምን”
ይላል እግዚአብሔር።

[25]“ ‘ሕልም አለምሁ! ሕልም አለምሁ!’ እያሉ በስሜ የሐሰት ትንቢት የሚናገሩትን የነቢያትን ቃል ሰምቻለሁ፤ [26]ይህ ነገር፣ የገዛ ልባቸውን ሽንገላ በሚተነብዩ በሐሰተኞች ነቢያት ልብ ውስጥ የሚቈየው እስከ መቼ ነው? [27]አባቶቻቸው በኣልን በማምለክ ስሜን እንደ ረሱ፣ እነርሱ በሚነጋገሩት ሕልም፣ ሕዝቤ ስሜን እንዲረሳ ያደረጉ ይመስላቸዋል። [28]ሕልመኛ ነቢይ ሕልሙን ያውራ፤ ቃሌ ያለው ግን በታማኝነት ይናገር፤ ገለባና እህል ምን አንድ አድርጎአቸው!” ይላል እግዚአብሔር። [29]“ቃሌ እንደ እሳት፣ ድንጋይንም እንደሚያደቅ መዶሻ አይደለምን?” ይላል እግዚአብሔር።

[30]“ስለዚህ ቃሌን እርስ በእርስ በመሰራረቅ ከእኔ እንደ ተቀበሉ አድርገው የሚናገሩትን ነቢያት እቃወማለሁ” ይላል እግዚአብሔር። [31]“አፈጮሌነታቸውን በመጠቀም፣ ‘እግዚአብሔር እንዲህ ይላል’ የሚሉትን ነቢያት እቃወማለሁ” ይላል እግዚአብሔር፤ [32]“እነሆ፤ ሐሰተኛ ሕልም ተመርኵዘው ትንቢት የሚናገሩትን ነቢያት እቃወማለሁ” ይላል እግዚአብሔር፤ እኔ ሳልልካቸው ወይም ሳልሾማቸው ደፍረው ውሸት ይናገራሉ፤ ሕዝቤንም ያስታሉ፤ ለዚህም ሕዝብ አንዳች አይረቡትም” ይላል እግዚአብሔር።

## የእግዚአብሔር ሸክም ምንድነው?

[33]“ይህ ሕዝብ ወይም ነቢይ ወይም ካህን፣ ‘የእግዚአብሔር ሸክም ምንድን ነው?’ ብለው ቢጠይቁ፣ ‘ሸክሙ እናንተ ናችሁ፤[a] እወረውራችኋለሁ ይላል እግዚአብሔር’ ብለህ መልስላቸው። [34]ነቢይ ወይም ካህን ወይም ማንኛውም ሰው፣ ‘የእግዚአብሔር ሸክም’ እያለ ቢናገር፣ ያን ሰውና ቤቱን እቀጣለሁ። [35]እያንዳንዱ ለባልንጀራው ወይም ለዘመዱ፣ ‘እግዚአብሔር ምን መልስ ሰጠ?’ ወይም፣ ‘እግዚአብሔር ምን ተናገረ?’ ማለት ይገባዋል። [36]ከእንግዲህ ግን፣ ‘የእግዚአብሔር ሸክም’ ብላችሁ መናገር አይገባችሁም፤ ምክንያቱም ለሰው ሁሉ የገዛ ራሱ ቃል ሸክሙ ስለሚሆን፣ የአምላካችንን የሰራዊት ጌታ የእግዚአብሔርን፣ የሕያው አምላክን ቃል ታጣምማላችሁ። [37]ስለዚህ ለነቢዩ፣ ‘እግዚአብሔር ምን መልስ ሰጠህ’ ወይም፣ ‘እግዚአብሔር ምን ተናገረህ?’ ትለዋለህ፤ [38]‘የእግዚአብሔር ሸክም’ ብትሉ እንኳ፣ እግዚአብሔር ግን እንዲህ ይላል፤ ‘እኔ፣ “የእግዚአብሔር ሸክም” አትበሉ ብዬ ብነግራችሁም፣ እናንተ፣ “የእግዚአብሔር ሸክም” ብላችኋል፤ [39]ስለዚህ እናንተን፣ እንዲሁም ለእናንተና ለአባቶቻችሁ የሰጠኋትን ከተማ ጭምር ፈጽሜ እተዋችኋለሁ፤ ከፊቴ እጥላችኋለሁ፤ [40]ለዘላለም የማይረሳ ዕፍረት፣ የዘላለምም ውርደት አመጣባችኋለሁ።

[a]33 ወይም ንግር፡ (ለንግር እና ለሸክም የሚተካው የዕብራይስጥ ቃል አንድ ዐይነት ነው)

23፥24 ዘፍ3፥8፤ነገ 8፥27፤ኢዮ11፥20፤ 22፥12-14፤መክ12፥14፤ኢሳ28፥15፤ 1ቆሮ4፥5
23፥25 ቍ16:28:32፤ዘዳ13፥1፤ኤር14፥14፤27፥9:10፤29፥8
23፥26 ኢሳ30፥10፤ ኤር14፥14፤ሕዝ13፥2 ፤1ጢሞ4፥1-2
23፥27 ዘዳ13፥1-3፤ መሳ3፥7፤8፥33-34፤ ኤር29፥8፤2፥23
23፥28 ቍ25፤ 1ሳሙ3፥17
23፥29 መዝ39፥3፤ ኤር5፥14፤1ቆሮ3፥13 ፤ዕብ4፥12
23፥30 ቍ2፤ዘዳ 18፥20፤መዝ34፥16፤ ኤር14፥15፤21፥13
23፥31 ቍ 17
23፥32 ቍ25:13፤ ኢዮ13፥4፤ኤር7፥8፤ 14፥14፤50፥6፤ሰቆ2፥ 14፤ሕዝ13፥3፤22፥28
23፥33 2ነገ21፥14፤ ሚል1፥1
23፥34 ሰቆ2፥14፤ ዘካ13፥3
23፥35 ኤር33፥3፤ 42፥4
23፥36 ኢሱ3፥10፤ ገላ1፥7-8፤2ጴጥ3፥16
23፥39 ኤር7፥15
23፥40 ኤር20፥11 ፤ሕዝ5፥14-15

23፥24 *እኔ እንዳላየው ... ሊሸሸግ፡* ኢዮ26፥6፤ መዝ139፥7-12፤ አሞ9፥2-4 ይመ። *ሰማይንና ምድርንስ የሞላሁ፤* ኢሳ66፥1 ይመ።

23፥25 *ሕልም፡* የእግዚአብሔር ሐሳብ ለእውነተኛ ነቢይ የሚገለጠው አብዛኛውን ጊዜ በሕልም አይደለም (27፥9፤ ዘዳ 13፥1-3፤ 1ሳሙ28፥6 ዘካ10፥2 ይመ፤ ሆኖም ከዘኍ12፥6፤ ከኢል 2፥28 ጋር ያነጻጽሩ)። *የሐሰት፡* 5፥12 ይመ። *በስሜ፤* ዘዳ 18፥20:22 ይመ።

23፥26 *ልባቸውን ... ልብ፤* በዕብራይስጥ እነዚህ ሁለት ቃላት አንድ ዐይነት መጠሪያ (ስም) አላቸው። *የገዛ ልባቸውን፡* የቍ16 ማብ ይመ።

23፥27 *ስሜን፡* የእግዚአብሔርን ስም መርሳት ማለት እግዚአብሔርን ራሱን እንደ መርሳት ነው። *በኣልን በማምለክ ... እንደ ረሱ፤* የቀድሞዎቹ የይሁዳ አባቶች በኣልን ማምለክና ማገልገል ሲጀምሩ፣ እግዚአብሔርን ይረሱ ነበር፤ በረሱ ቍጥርም ለበኣል የነበራቸው ታማኝነት እየጠነከረ ይሄድ ነበር (መሳ3፥7፤ 1ሳሙ12፥9-10 ይመ)።

*23፥28-29፤* እውነተኛው የእግዚአብሔር ቃል በሦስት ዐይነት ዘይቤአዊ አነጋገር ተገልጦአል (እህል፣ እሳት፣ መዶሻ)።

23፥28 *ገለባና እህል፤* ከሁለቱ ለምግብ የሚሆነውና ሰውነትን የሚያለመልመው እህል ብቻ ነው (የ15፥16 ማብ ይመ)።

23፥29 *እንደ እሳት፡* የ20፥9 ማብ ይመ። መጨረሻ ላይ፣ “የእያንዳንዱን ሰው ተግባር ምንነት ለይቶ የሚገልጸው” የእግዚአብሔር ቃል እሳት ነው (1ቆሮ3፥13 ይመ)። *እንደሚያደቅ መዶሻ፡* የእግዚአብሔር ቃል ያለ ርኅራኄ እንደ ሰይፍ ወይም እንደ መዶሻ ሆኖ በመሥራት “የሰውን የልብ ስሜትና ሐሳብ” በመመርመር በመጨረሻ ላይ ፈራጅ ይሆናል (ዕብ4፥12 ይመ)።

23፥30-32 *እቃወማለሁ፤* ይህ አባባል በእነዚህ ሦስት ቍጥሮች ተደጋግሞ መጠቀሱ አጽንዖት ለመስጠት ነው (የ22፥29 ማብ ይመ)።

23፥31 ... *የሚሉትን ነቢያት፤* ሐሰተኞቹ ነቢያት፣ የሚናገሩትን የትንቢት ቃል ከእግዚአብሔር እንደ ተቀበሉ አድርገው ያቀርባሉ። “የሚሉት” ለሚለው የገባው የዕብራይስጥ ግስ ከእግዚአብሔር ውጭ ጥቅም ላይ የዋለው እዚህ ላይ ብቻ ነው፤ “ይላል እግዚአብሔር” የሚለው ሐረግ በብሉይ ኪዳን ውስጥ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል፤ ተደጋግሞ በብዛት የሚገኘው ግን በትንቢተ ኤርምያስ ውስጥ ነው (ከ175 ጊዜ በላይ)።

23፥32 *ሳልልካቸው፤* ቍ21 እና ማብ ይመ።

23፥33 *ሸክም፡* በዕብራይስጡም ይህ ቃል “ሸክም” ማለት ሲሆን፣ ከጌታ የሆነ ከባድ መልእክትን ያሳያል (ለምሳሌ:- ናሆ 1፥1 ይመ)።

*23፥36፤* በቍጥሩ መጨረሻ ላይ ሦስቱ የእግዚአብሔር መጠሪያ ስሞች መጠቀሳቸው በቍጥሩ ላይ የተላለፈው መልእክት የቱን ያህል ክቡር እንደ ሆነ ለመግለጽ ነው። *የሕያው አምላክን፤* 10፥10፤ ዘዳ5፥26 ይመ።

23፥39 *እተዋችኋለሁ፤* ለዚህ ቃል የገባው የዕብራይስጡ ቃል “ሸክም” በሚል አሳቤ ከገባው የዕብራይስጥ ቃል ጋር ተመሳሳይ የሆነ ድምፅ አለው (“ሸክም” የሚለው ቃል በቍ33-34:36:38 ላይ ገብቶ ይገኛል)። *ከተማ፤* ኢየሩሳሌምን ነው።

*24፥1-10፤* አሞ8፥1-3 ይመ። ኤርምያስ የይሁዳን መሪዎች ዐመፅ ገልጾ ከተናገረ በኋላ (21፥1-23፥8)፣ ሐሰተኞች ነቢያትንም ካጋለጠ በኋላ (23፥9-40)፣ አሁን ደግሞ የይሁዳን ሕዝብ ጥሩና መጥፎ በማለት በሁለት ይከፍላቸዋል (24፥1-3)፤ በመቀጠልም እግዚአብሔር መልካሙን ሕዝብ መልሶ እንደሚያቋቍም (ቍ4-7) መልካም ያልሆነውን መጥፎ ሕዝብ ግን ለማጥፋት (ቍ8-10) እንደ ወሰነ ባጭሩ ያቀርባል። መልካም የተባሉት ሕዝብ በሙሉ ልባቸው ወደ እግዚአብሔር የሚመለሱና ባዕድ አምልኮን የሚያስወግዱ ይሆናሉ (ቍ7)፤ እግዚአብሔርም ዓለምን የማዳን ዓላማውን በዚሁ ሕዝብ አማካይነት ይፈጽማል።

## መልካሙና መጥፎው በለስ

**24** የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር፣ የኢዮአቄምን ልጅ የይሁዳን ንጉሥ ኢኮንያንንና[a] ባለሥልጣኖቹን እንዲሁም የይሁዳን አናጺዎችና ብረት ቀጥቃጮች ከኢየሩሳሌም ወደ ባቢሎን ማርኮ ከወሰዳቸው በኋላ፣ *እግዚአብሔር* ሁለት ቅርጫት በለስ *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ፊት ለፊት ተቀምጦ አሳየኝ:: [2]አንዱ ቅርጫት፣ ቶሎ የደረሰ ፍሬ የሚመስል እጅግ መልካም በለስ ነበረበት፣ በሌላው ቅርጫት ግን ከመበላሸቱ የተነሣ ሊበላ የማይቻል እጅግ መጥፎ በለስ ነበረበት::

[3]*እግዚአብሔርም*፣ "ኤርምያስ ሆይ፤ የምታየው ምንድን ነው?" አለኝ::

እኔም፣ "በለስን አያለሁ፤ ጥሩ የሆነው እጅግ መልካም ነው፤ የተበላሸው ግን እጅግ መጥፎ በመሆኑ ሊበላ የማይችል ነው" አልሁ::

[4]እንደ ገናም *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ፤ [5]"የእስራኤል አምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'እንደዚህ እንደ መልካሙ በለስ፣ ከዚህ ስፍራ ወደ ባቢሎናውያን[+] ምድር የሰደድሁትን የይሁዳ ምርኮ በመልካም አስበዋለሁ:: [6]ዐይኔን ለበጎነት በእነርሱ ላይ አደርጋለሁ፤ ወደዚህችም ምድር እመልሳቸዋለሁ፤ እሠራቸዋለሁ እንጂ አላፈርሳቸውም፤ እተክላቸዋለሁ እንጂ አልነቅላቸውም:: [7]እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ የሚያውቅ ልብ እሰጣቸዋለሁ፤ በፍጹም ልባቸውም ወደ እኔ ስለሚመለሱ፣ እነርሱ ሕዝብ ይሆኑኛል፤ እኔም አምላክ እሆናቸዋለሁ::

[8]" 'ነገር ግን ከመበላሸቱ የተነሣ ሊበላ እንደማይቻለው እንደ መጥፎ በለስ' ይላል *እግዚአብሔር*፤ 'የይሁዳን ንጉሥ ሴዴቅያስን ባለሥልጣኖቹን እንዲሁም በኢየሩሳሌም የቀሩትንም ሆነ በግብፅ የሚኖሩትን፣ እንዲሁ አደርግባቸዋለሁ:: [9]በምድር መንግሥታት ሁሉ ፊት የሚያስጸይፉና የሚሰደቡ ይሆናሉ፤ በምበትናቸውም ስፍራ ሁሉ ለማላገጫና ለመተረቻ፣ ለመሣለቂያና ለርግማን አደርጋቸዋለሁ:: [10]ለእነርሱና ለአባቶቻቸው ከሰጠኋቸው ምድር እስኪጠፉ ድረስ ሰይፍ፣ ራብና መቅሠፍት እሰድባቸዋለሁ::

## ሰባ የምርኮ ዓመታት

**25** የይሁዳ ንጉሥ የኢዮስያስ ልጅ ኢዮአቄም በነገሠ በአራተኛው ዓመት፣ ይህም ማለት በባቢሎን ንጉሥ በናቡከደነፆር ዘመነ መንግሥት በመጀመሪያው ዓመት፣ ስለ ይሁዳ ሕዝብ ሁሉ ለኤርምያስ ቃል መጣለት፤ [2]ስለዚህ ነቢዩ ኤርምያስ ለይሁዳ ሕዝብ ሁሉ፣ በኢየሩሳሌም ለሚኖሩትም ሁሉ እንዲህ ሲል ተናገረ:- [3]የይሁዳ ንጉሥ የአሞን ልጅ ኢዮስያስ ከነገሠበት ከዐሥራ ሦስተኛው ዓመት ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ ሃያ ሦስት ዓመት ሙሉ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ እኔ መጣ፤ ደጋግሜም ነገርኋችሁ፤ እናንተ ግን አልሰማችሁም::

[a]1 በዕብራይስጡ *ኢኮንያን፣ የኢዮአኪን* አቻ ስም ነው::
[+]5 ወይም *ከለዳውያን*

24፥1 ዘፀ23፥19፤ ዘዳ26፥2፤2ነገ24፥16፤ 2ዜና36፥9፤አሞ8፥1-2
24፥2 መሐ2፥13፤ ኢሳ5፥4
24፥3 ኤር1፥11፤ አሞ8፥2
24፥5 ኤር29፥4:20
24፥6 ዘዳ30፥3:9፤ ኤር1፥10፤27፥22፤ 29፥10፤30፥3፤33፥7፤ 42፥10፤ሕዝ11፥17፤ አሞ9፥14-15
24፥7 ዘሌ26፥12፤ 2ዜና6፥37፤ኢሳ11፥9፤ 51፥16፤ኤር32፥40፤ ሕዝ11፥19፤ዘካ2፥11 ፤ዕብ8፥10
24፥8 ኤር29፥17፤ 32፥4-5፤38፥18:23፤ 39፥5:6:9፤44፥1:26: 30፤46፥14
24፥9 ዘዳ28፥25:37 ፤1ነገ9፥7፤2ነገ22፥19፤ ኤር15፥4፤25፥18፤ 29፥18፤ዳን 9፥7
24፥10 ዘዳ28፥21፤ ኢሳ51፥19፤ኤር9፥16 ፤15፥2፤27፥8፤ራእ6፥8
25፥1 2ነገ24፥1:2
25፥2 ኤር18፥11
25፥3 1ዜና3፥14፤ ኢሳ65፥12፤ኤር 7፥26፤11፥7፤26፥5

24፥1 *ኢኮንያንንና ባለሥልጣኖቹን ... ማርኮ ከወሰዳቸው በኋላ፤* ይህ የሆነው በ597 ዓ.ቅ.ክ. ነበር:: *አናጺዎችና ብረት ቀጥቃጮች፤* 29፥2፤ 2ነገ24፥14:16 ይመ:: በይሁዳ ምድር እንዲቀሩ የተደረጉት እጅግ ድኾችና ደካሞች ሰዎች ብቻ ነበሩ (2ነገ24፥14 ይመ):: *እግዚአብሔር ... አሳየኝ፤* ትንቢት ለመናገር የሚያስችሉ ራእዮችን የተቀበሉ ነቢያት ያዩትን ለሰዎች የሚገልጹበት የተለመደ አቀራረብ ነው (አሞ7፥1:4:7 ይመ):: *በለስ፤* የ8፥13 ማብ ይመ:: *ተቀምጦ፤* በዕብራይስጡ የዚህ ቃል አመጣጥ በዘፀ29፥42-43 "መገናኘት" በሚል ተተርጕሞ አል፤ እግዚአብሔር ሕዝቡን እስራኤልን በመገናኛው ድንኳን ደጃፍ ሊገናኛቸው እንደ ወደደ፣ የይሁዳን ሕዝብ የሚወክለውን በለስም በኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ መግቢያ ደጅ "መገናኘት" ነበረበት::

24፥2 *ቶሎ የደረሰ ... እጅግ መልካም በለስ፤* በሰኔ ወር ገደማ የሚደርስ የመጀመሪያው የበለስ ፍሬ ውሃ ያለውና ጣዕመ ጣፋጭ ነው (ኢሳ28፥4፤ ሆሴ9፥10፤ ሚክ7፥1፤ ናሆ3፥12 ይመ)::

24፥3 *የምታየው ምንድን ነው?* የ1፥11 ማብ ይመ::

*24፥5-6፤* መልካም የበለስ ፍሬን ባለቤቱ እንደሚንከባከበውና እንደሚጠነቀቅለት፣ በ597 ዓ.ቅ.ክ በምርኮ ለተጋዙት ምርጥ የይሁዳ ባለሥልጣናትና የእጅ ጥበብ ላላቸው ሰዎች (2ነገ24፥14-16 ይመ) እግዚአብሔር ይጠነቀቃል፤ ጥበቃም ያደርግላቸዋል (29፥4-14 ይመ)::

24፥6 *ዐይኔን ለበጎነት በእነርሱ ላይ አደርጋለሁ፤* ከአሞ9፥4 ጋር ያገናዝቡ:: *እመልሳቸዋለሁ፤* ይህ የተፈጸመው በ538 ዓ.ቅ.ክ ነበር:: *እሠራቸዋለሁ ... አላፈርሳቸውም ... እተክላቸዋለሁ ... አልነቅላቸውም፤* 1፥10 እና ማብ ይመ::

24፥7 *እኔ ... እንደ ሆንሁ የሚያውቅ ልብ፤* ተመሳሳይ የተስፋ ቃል ኖሮበት ሰፋ ባለ መልክ የቀረበውን ትንቢያ 31፥31-34 ላይ ይመ:: *ሕዝብ/ ይሆኑኛል ... አምላክ እሆናቸዋለሁ፤* የተለመደና የማይሻር የኪዳን ግንኙነት መግለጫ ነው (31፥33፤ 32፥38 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፍ17፥7፤ የዘካ8፥8 ማብ ይመ):: *በፍጹም ልባቸውም፤* 29፥13 ይመ::

24፥8 *በግብፅ የሚኖሩትን፤* ከንጉሡ ከኢዮአካስ ጋር በ609 ዓ.ቅ.ክ ወደዚያ የተወሰዱ ሊሆኑ ይችላሉ (22፥10-12 እና ማብ፤ 2ነገ23፥31-34 ይመ)፤ ወይም ባቢሎናውያን ግብፃውያንን በ605 ዓ.ቅ.ክ በከርከሚሽ ድል ካደረጉ በኋላ ወደዚያ የተወሰዱ ሊሆኑ ይችላሉ፤ ወይም በሁለቱም ጊዜያት የተወሰዱ ሊሆኑ ይችላሉ (46፥2 ይመ)::

24፥9 *በ ... መንግሥታት ሁሉ ፊት የሚያስጸይፉና፤* 34፥17 ይመ:: *ለማላገጫና ... ለመሣለቂያና፤* ዘዳ28፥37 ይመ:: *ለመተረቻ፤* የ1ነገ9፥7፤ የኢዮ17፥6 ማብ ይመ::

24፥10 *ሰይፍ፣ ራብና መቅሠፍት፤* የ14፥12 ማብ ይመ:: *ከ ... ምድር እስኪጠፉ ድረስ፤* ይህ በ586 ዓ.ቅ.ክ የተፈጸመውን የሚያመለክት ነው (52፥4-27 ይመ)::

*25፥1-29፥32፤* በም25-29 ውስጥ ጕልቶ የሚታየው ሐሳብ ሊመጣ ያለው የኢየሩሳሌም ከተማ መውደምና የሕዝቡ ወደ ባቢሎን ምድር በምርኮ መጋዝ ነው፤ ይህም የሚሆነው በ586 ዓ.ቅ.ክ ሲሆን፣ በ24፥10 ላይ ፍንጩ ይታያል::

25፥1-38፤ የእግዚአብሔር ቍጣ የሚነሣሣውና ፍርዱ የሚመጣው በይሁዳ ላይ ብቻ ሳይሆን፣ "በአካባቢዋ ባሉ ሕዝቦች ሁሉ ላይ" ጭምር ነበር (ቍ9)::

25፥1 *ኢዮአቄም በነገሠ በአራተኛው ዓመት፣ ... በናቡከደነፆር ... በመጀመሪያው ዓመት፤* የሁለቱ ነገሥታት ዘመን በተጠቀሰው ዓመት መሠረት ሲገናዘብ፣ ያ ዘመን 605 ዓ.ቅ.ክ ይሆናል (የዳን1፥1 ማብ ይመ)::

25፥3 *ሃያ ሦስት ዓመት፤* ዐሥራ ዘጠኙ ዓመት በኢዮስያስ የግዛት ዘመን ሥር ሲሆን፣ አራቱ ደግሞ በኢዮአቄም ዘመን ነበር (ቍ1 ይመ):: *ኢዮስያስ ከነገሠበት ከዐሥራ ሦስተኛው ዓመት ጀምሮ፤* ከ626 ዓ.ቅ.ክ ጀምሮ ማለት ነው፤ ወይም አንድ ዓመት ቀደም ብሎ በ627 ዓ.ቅ.ክ ሊሆን ይችላል፤ 1፥2 ይመ:: *ደጋግሜም፤* ቍ4 ይመ፤ በተጨማሪም የ7፥13 ማብ ይመ:: *አልሰማችሁም፤* ኤርምያስ በዚህ ጊዜ የነቢይነቱን አገልግሎት አጋምሶአል፤ የይሁዳ ሕዝብ እንደሚቃወመውና እምቢተኛ እንደሚሆንበትም ገና ወደ አገልግሎቱ ሲመጣ ተነግሮታል (1፥17-19

[4]*እግዚአብሔር* አገልጋዮቹን ነቢያትን ሁሉ ደጋግሞ ወደ እናንተ ላከ፤ ሆኖም አልሰማችሁም፤ ትኩረትም አልሰጣችሁትም። [5]እነርሱም እንዲህ አሉ፤ "እንግዲህ ሁላችሁ ከክፉ መንገዳችሁና ከክፉ ሥራችሁ ተመለሱ፤ *እግዚአብሔር* ለእናንተና ለአባቶቻችሁ በሰጣት ምድር ለዘላለም ትቀመጣላችሁ። [6]ታገለግሏቸውና ታመልኳቸው ዘንድ ሌሎቹን አማልክት አትከተሉ፤ እጃችሁ በሠራው ነገር አታስቈጡኝ፤ እኔም ክፉ አላደርግባችሁም።"

[7]"ነገር ግን አልሰማችሁኝም" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "እጃችሁ በሠራው ነገር አስቈጣችሁኝ፤ በራሳችሁም ላይ ክፉ ነገር አመጣችሁ።"

[8]ስለዚህ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ቃሌን ስላልሰማችሁ፣ [9]የሰሜንን ሕዝብ ሁሉ፣ አገልጋዬንም የባቢሎንን ንጉሥ ናቡከደነፆርን እጠራለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "በዚህች ምድርና በነዋሪዎቿም ላይ፣ በአካባቢዋም ባሉ ሕዝቦች ሁሉ ላይ አመጣባቸዋለሁ፤ ፈጽሜም አጠፋቸዋለሁ፤[a] ሰዎች የሚጸየፉአቸውና የሚሣለቁባቸው፣ የዘላለምም ባድማ አደርጋቸዋለሁ፤ [10]የደስታንና የእልልታን ድምፅ፣ የሙሽራውንና የሙሽራዪቱን ድምፅ፣ የወፍጮን ድምፅና የመብራትን ብርሃን አስቀራለሁ። [11]አገሪቱ በሞላ ባድማና ጠፍ ትሆናለች፤ እነዚህም ሕዝቦች ለባቢሎን ንጉሥ ሰባ ዓመት ይገዛሉ።

25፥4 ኤር6፥17፤ 7፥25፡26፤29፥19፤ 34፥14፤44፥5
25፥5 ዘፍ12፥7፤ዘዳ 4፥40፤መሳ6፥8፤2ዜና 7፥14፤30፥9፤ኤር 23፥22
25፥6 ዘፀ20፥3፤ዘዳ 8፥19
25፥7 ዘዳ32፥21፤ 2ነገ17፥20፤21፥15፤ ኤር30፥14፤32፥35 44፥5
25፥9 ዘኍ21፥2፤ 2ዜና29፥8፤36፥6፤ኢሳ 13፥3-5፤14፥31፤41፥2 ፤ኤር19፥8፤20፥4፤ 27፥6፤ሕዝ12፥20
25፥10 ኢዮ18፥5፤ መክ12፥3-4፤ኢሳ 24፥8፤ኤር7፥34፤33፥ 11፤ሰቆ5፥15፤ሕዝ26፥ 13፤ራእ18፥22-23
25፥11 ዘሌ26፥31-32፤2ዜና36፥21፤ኤር 4፥26-27፤12፥11-12፤ 28፥14
25፥12 ዘፍ10፥10፤ መዝ137፥8፤ኢሳ13፥ 19-22፤14፥22-23፤ ኤር27፥7፤29፥10
25፥13 ኢሳ30፥8
25፥14 ዘዳ32፥41፤ ኢዮ21፥19፤ኢሳ14፥6 ፤ኤር27፥7፤50፥9፤ 51፥6፡27-28
25፥15 ኢሳ51፥17፤ ኤር1፥5፤49፥12፤ሰቆ 4፥21፤ሕዝ23፥31፤ ራእ14፥10

[12]"ነገር ግን ሰባው ዓመት ከተፈጸመ በኋላ፣ የባቢሎንን ንጉሥና ሕዝቡን፣ የባቢሎናውያንንም[+] ምድር ስለ በደላቸው እቀጣቸዋለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "ለዘላለምም ባድማ አደርጋታለሁ፤ [13]በምድሪቱ ላይ የተናገርሁትን ሁሉ ይኸውም በዚህ መጽሐፍ የተጻፈውንና ኤርምያስ በሕዝቦች ሁሉ ላይ የተናገረውን ትንቢት አመጣባታለሁ። [14]ሕዝቧም ለብዙ ሕዝቦችና ለታላላቅ ነገሥታት ባሮች ይሆናሉ፤ እንደ አድራጎታቸውና እንደ እጃቸውም ሥራ እከፍላቸዋለሁ።"

### የቍጣው ጽዋ

[15]የእስራኤል ስምባለ *እግዚአብሔር* እንዲህ አለኝ፤ "በቍጣዬ የወይን ጠጅ የተሞላውን ይህን ጽዋ ከእጄ ውሰድ፤ እኔ ወደምልክህም ሕዝቦች ሁሉ ሄደህ አጠጣቸው። [16]በጠጡም ጊዜ ይንገዳገዳሉ፤ በመካከላቸው ከምሰደው ሰይፍ የተነሣ ያብዳሉ።"

[17]ስለዚህ ጽዋውን *ከእግዚአብሔር* እጅ ተቀብዬ እርሱ ወደ ላከኝ ሕዝቦች ሁሉ ሄድሁ፤ እንዲጠጡትም አደረግሁ፤ [18]ዛሬ እንደ ሆነው ሁሉ ባድማና ሰዎች የሚጸየፉአቸው መዘባበቻና ርግማን እንዲሆኑ፦ ኢየሩሳሌምንና የይሁዳን ከተሞች፣

[a]9 *አጠፋቸዋለሁ* ለሚለው የሚተካው የዕብራይስጥ ቃል የሚያመለክተው ነገሮች ወይም ሰዎች (ደግሞ ላይመለሱ) ለእግዚአብሔር ሙሉ በሙሉ መስጠታቸውን ነው።
[+]12 ወይም *ከለዳውያን*

*ይመ*)።

*25፥4፤* በ7፥25-26 ላይ ያለውን ሐሳብ የሚያንጸባርቅ ነው፤ በተጨማሪም 35፥15 *ይመ*። አገልጋዮቹን ነቢያትን፤ የ7፥25 ማብ *ይመ*።

25፥5 *እግዚአብሔር ... ለአባቶቻችሁ በሰጣት ምድር ለዘላለም ትቀመጣላችሁ፤* የ7፥7 ሐሳብ እዚህ ላይ ተንጸባርቆ ይገኛል፤ ዘፍ17፥8 እና ማብ *ይመ*።

25፥6 *አታስቈጡኝ፤* 7፥18፤ ዘዳ31፥29 *ይመ*። *እጃችሁ በሠራው ነገር፣* የጣዖታት ምስል ማለት ነው (የ 1፥16 ማብ *ይመ*)።

25፥7 *በራሳችሁም ላይ ክፉ ነገር አመጣችሁ፤* 7፥6 *ይመ*።

25፥9 *የሰሜንን ሕዝብ፣* ባቢሎንንና አጋሮቿን የሚያጠቃልል ነው (1፥15 እና ማብ *ይመ*)። *አገልጋዬንም ... ናቡከደነፆርን፤* 27፥6፤ 43፥10 *ይመ*። እዚህ ላይ "አገልጋይ" የሚለው ቃል "እግዚአብሔርን አምኖ ተቀብሎ ማገልገልን" ሳይሆን፣ "ጕዳይ ፈጻሚና ተላላኪ አገልጋይ" ወይም "ፍርድ በእርሱ አማካይነት የሚፈጸምበት አገልጋይ" ለማለት ነው፤ ይኸውም አረማዊው ንጉሥ ቂሮስ በኢሳ44፥28 የጌታ "እረኛ"፣ በኢሳ45፥1 ደግሞ "የተቀባ" እንደ ተባለው ነው። *በዚህችም ምድርና፣* የይሁዳን ምድር ማለት ነው። *በአካባቢዋም ባሉ ሕዝቦች፣* በቍ19-26 ስም ዝርዝራቸው ተለይቶ ታውቋል። *ፈጽሜም አጠፋቸዋለሁ፤* የዕብራይስጡ አባባል በማያዳግም ሁኔታ ለእግዚአብሔር ክብር ሲባል፣ ከቍጣው የተነሣ አንድን ነገር ወይም ሰው ማጥፋትን የሚያመለክት ነው፤ 50፥21፡26፤ 51፥3 *ይመ*፤ በተጨማሪም የዘዳ2፥34 ማብ *ይመ*። *ሰዎች የሚጸየፉአቸውና የሚሣለቁባቸው፣* የ18፥16 ማብ *ይመ*። *ለዘላለምም ባድማ፤* 49፥13፤ መዝ74፥3፤ ኢሳ58፥12 እና ማብ *ይመ*።

25፥11-12 *ሰባ ዓመት፣* 29፥10 *ይመ*። ይህ ከሞላ ጐደል በማጠጋጋት የተጠቀሰው አኃዝ (በመዝ90፥10፤ በኢሳ 23፥15 እንደ ተጠቀሰው) ምናልባት ከ605 ዓ.ቅ.ክ (የቍ1፤ የዳን1፥1 ማብ *ይመ*) እስከ 538 ዓ.ቅ.ክ ያለውን ጊዜ የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም፤ ይህ ወቅት የይሁዳ ሕዝብ ከምርኮ መመለስ የጀመረበትን ጊዜ ያሳያል (2ዜና36፥20-23 *ይመ*፤ እንዲሁም የዳን9፥1-2 ማብ *ይመ*)። ዘካ1፥12 ላይ ያለው 'ሰባ ዓመት'፣ እዚህና በ29፥10 ላይ ያለው 'ሰባ ዓመት' አንድ ናቸው ማለት አይቻልም። ከ586 ዓ.ቅ.ክ (ንጉሥ ሰሎሞን ያሠራው ቤተ መቅደስ የወደመበት ጊዜ) እስከ 516 ዓ.ቅ.ክ (ዘሩባቤል የቤተ መቅደሱን ሥራ የጨረሰበት ጊዜ) ድረስ ያለውን ጊዜ ሳያመለክት አይቀርም፤ የዘካ7፥5 ማብ *ይመ*።

25፥11 *አገሪቱ ... እነዚህም ሕዝቦች፤* የይሁዳ ምድርና በቍ19-26 ላይ ስማቸው የተጠቀሰው አሕዛብ ማለት ነው።

25፥12 *የ... ንጉሥና ሕዝቡን ... እቀጣቸዋለሁ፤* 50፥18 *ይመ*። የባቢሎን ከተማ በ539 ዓ.ቅ.ክ በሜዶናውያንና በፋርስ ሰዎች እጅ ወድቃለች (ይኸውም ኤርምያስ የተናገረው ሰባ ዓመት ማብቂያ አካባቢ ነበር፤ የቍ11-12 ማብ *ይመ*)። *ስለ በደላቸው፣* 50፥11፡31-32፤ 51፥6፡49፡53፡56፤ ኢሳ13፥19 *ይመ*። *ለዘላለምም ባድማ አደርጋታለሁ፤* 50፥12-13፤ 51፥26 *ይመ*፤ በተጨማሪም የኢሳ13፥20 ማብ *ይመ*።

25፥13 *መጽሐፍ፤* ልክ ከዚህ ቃል በኋላ የግሪኩ የብሉይ ኪዳን ትርጕም (የሰባ ሊቃናት ትርጕም) ከም46-51 ያለውን ክፍል አስገብቶ ይገኛል፤ ሆኖም ቅደም ተከተሉ ቀድሞ ከነበረው ይለያል።

25፥14 *ለብዙ ሕዝቦችና፤* ሜዶን፣ ፋርስና አጋሮቻቸውን ማለት ነው። *ታላላቅ ነገሥታት፤* ቂሮስንና ግብረ አበሮቹን ነው። *እንደ አድራጎታቸውና ... እከፍላቸዋለሁ፤* 50፥29፤ 51፥24 *ይመ*።

25፥15 *በቍጣዬ የወይን ጠጅ የተሞላውን ይህን ጽዋ፣* በተለይ በክፉዎች አሕዛብ ላይ የሚደርሰውን የእግዚአብሔርን ፍርድ የሚያመለክት ነው (ኢሳ51፥17 እና ማብ *ይመ*፤ በተጨማሪም 51፥7፤ ራእ18፥6 *ይመ*)። *ወደ ምልክህም ሕዝቦች፣* 1፥5 እና ማብ *ይመ*።

25፥16 *ይንገዳገዳሉ ... ያብዳሉ፤* 13፥12-14 እና ማብ፤ ራእ14፥8 *ይመ*። *ከ ... ሰይፍ የተነሣ፤* በጠጅ የሰከረ እንደሚንገዳገድና እንደሚወድቅ ሁሉ፣ የወጋቸው ሰይፍ ይጥላቸዋል፤ ከቶም አይነሡም (ቍ27 *ይመ*)።

*25፥17፤* በአሕዛብ ላይ ስለሚመጣው የእግዚአብሔር ፍርድ፣ ኤርምያስ መናገሩን ያመለክታል።

25፥18 *ኢየሩሳሌምንና የይሁዳን፤* ፍርዱ ከሁሉ አስቀድሞ የሚመጣው በራሱ በእግዚአብሔር ሕዝብ ላይ ነው (ቍ29 *ይመ*፤

ነገሥታቷንና ባለሥልጣኖቿን፣ [19]የግብፅን ንጉሥ ፈርዖንን፣ አገልጋዮቹን፣ ባለሥልጣ ኖቹንና ሕዝቡን ሁሉ፣ [20]በዚያ የሚኖሩትን ድብልቅ ሕዝብ ሁሉ፣ የዖፅ ምድር ነገሥታ ትን ሁሉ፣ በአስቀሎናና፣ በጋዛ፣ በአቃሮንና በአዛጦንም ሕዝብ ቅሬታ ያሉትን የፍልስ ጥኤም ነገሥታት፣ [21]ኤዶምን፣ ሞዓብን፣ አሞንን፣ [22]የጢሮስንና የሲዶናን ነገሥታት ሁሉ፣ ከባሕሩ ማዶ ያሉ የጠረፍ ምድር ነገሥታትን፣ [23]ድዳንን፣ ቴማንን፣ ቡዝ ን፣ ጠጕራቸውን ዙሪያውን የሚከረከሙ ትን ሕዝብ ሁሉ፣[*] [24]የዐረብ ነገሥታትን ሁሉ፣ በምድረ በዳ የሚኖሩትን የድብ ልቅ ሕዝብ ነገሥታት ሁሉ፣ [25]የዘምሪ፣ የኤላምና የሜዶን ነገሥታትን ሁሉ፣ [26]በቅ ርብና በሩቅ ያሉትን የሰሜን ነገሥታትንም ሁሉ በማከታተል፣ በምድር ላይ ያሉትን መን ግሥታት ሁሉ አጠጣኋቸው፤ ከእነዚህም ሁሉ በኋላ የሺሻክ[†] ንጉሥ ደግሞ ይጠጣል።

[27]"አንተም እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ 'የእ ስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል:- ጠጡ፤ ስከሩ፤ አስታውኩም፤ ዳግመኛም ሳትነሡ በመካከላችሁ በምሰደው ሰይፍ ፊት ውደቁ።' [28]ነገር ግን ጽዋውን ከእጅህ ለመውሰድና ለመጠጣት እንቢ ካሉ፣ እንዲህ በላቸው:- 'የሰራዊት ጌታ እግዚ አብሔር እንዲህ ይላል፤ በግድ ትጠጣላ ችሁ። [29]እነሆ፤ ስሜ የተጠራበትን ከተማ ማጥፋት እጀምራለሁ፤ ታዲያ ያለ ቅጣት ታመልጣላችሁን? ሳትቀጡ አትለቀቁም፤ በምድር በሚኖሩት ሁሉ ላይ ሰይፍን እጠ ራለሁና ሳትቀጡ አታመልጡም፤ ይላል የሰ ራዊት ጌታ እግዚአብሔር።'

[30]"እንግዲህ ይህን ቃል ሁሉ ትንቢት ተናገርባቸው፤ እንዲህም በላቸው፣

"'እግዚአብሔር ከላይ ይጮኻል፤
ከቅዱስ ማደሪያው ነጐድጓዳማ ድምፁን
ያሰማል፤
በራሱ ምድር ላይ እጅግ ይጮኻል፤
እንደ ወይን ጨማቂዎች፣
በምድር በሚኖሩት ሁሉ ላይም
ያስገመግማል፤
[31]እግዚአብሔር ከሕዝቦች ጋር ይፋረዳልና፣
ታላቅ ጩኸት እስከ ምድር ዳርቻ
ያስተጋባል፤
በሰው ሁሉ ላይ ፍርድን ያመጣል፤
ከፉዎችንም ለሰይፍ ይዳርጋል"
ይላል እግዚአብሔር።

[32]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

"እነሆ፤ ጥፋት፣
ከአገር ወደ አገር እየተዛመተ
መጥቶአል፤
ብርቱ ዐውሎ ነፋስ፣

25፥16 ቍ26-29፤ መዝ60፥3፤ኤር51፥7
25፥17 ኤር1፥10፤ 27፥3
25፥18 ዘፍ19፥13፤ ኢዮ12፥19፤2ዜና 29፥8፤ኤር13፥13፤ 24፥9፤44፥22
25፥19 2ነገ18፥21፤ ኢሳ19፥1፤20፥3፤ኤር 44፥30፤ሕዝ29፥2
25፥20 ዘፍ10፥19: 23፤ኢሱ13፥3፤2ዜና 26፥6፤28፥18፤ኤር 47፥5፤አሞ1፥7-8፤ ሶፎ2፥4-7
25፥21 ዘፍ25፥30 ፤19፥37:38፤ዘዳ23፥6 ፤ኤር27፥3፤49፥1
25፥22 ዘፍ10፥15፤ ኢሱ19፥29፤ኢሳ 11፥11፤48፥20፤66፥ 20፤ኤር31፥10፤ሕዝ 27፥15፤39፥6፤ዳን 11፥18
25፥23 ዘፍ22፥21፤ 25፥3:15፤ኤር9፥26፤ 49፥32
25፥24 ቍ20፤2ዜና 9፥14
25፥25 ዘፍ10፥22፤ 25፥2፤ኢሳ21፥2
25፥26 ቍ9፤ኢሳ 23፥17፤ኤር50፥3:9፤ 51፥11:41:48
25፥27 ቍ16:28፤ ኢሳ29፥9፤49፥26፤ ኤር12፥12፤51፥57፤ ሕዝ14፥17፤21፥4፤ 23፥32-34፤ናሆ3፥18 ፤ዕን2፥16
25፥28 ኢሳ51፥23
25፥29 ቍ27:30-31፤ዘዳ28፥10፤2ሳሙ5፥7፤ምሳ11፥31፤ኢሳ 10፥12፤24፥1፤34፥2፤37፥17፤ኤር13፥12-14፤39፥1 25፥30 ኢሳ 16፥10፤42፥13፤63፥3፤መዝ46፥6፤68፥5፤ኢል3፥13፤ራእ14፥19-20
25፥31 ቍ29፤1ሳሙ12፥7፤ኤር2፥9:35፤15፥9፤23፥19፤ሕዝ36፥5
25፥32 ዘዳ28፥49፤ኢሳ30፥25፤34፥2፤ኤር23፥19

[*]23 *ወይም በሩቅ ስፍራዎች ያሉትን*
[†]26 *ሺሻክ* የባቢሎን ምስጢራዊ ቃል ነው።

በተጨማሪም ሕዝ9፥6፤ 1ጴጥ4፥17 ይመ)። *ነገሥታቷንና፤* የ17፥20 ማብ ይመ። *ባድማና ሰዎች የሚጸየፉአቸው መዘባበቻና እርግማን፤* ቍ9:11፤ 18፥16፤ 19፥8 ይመ።

25፥19-26፤ በም 46፥51 እንዳለው ሁሉ፣ የመንግሥታቱ ዝርዝር በግብፅ ጀምሮ በባቢሎን ያበቃል፤ ደማስቆ ግን (49፥23-27 ይመ) ተዘሉአል፤ ሌሎች ጥቂቶች ቦታዎች ደግሞ ተጨም ረዋል።

25፥19 *የግብፅን፤* 46፥2-28 ይመ።

25፥20 *ድብልቅ ሕዝብ፤* ቍ24፤ ነህ13፥3 ይመ። *የፅ፤* የኢዮ1፥1 ማብ ይመ። *ፍልስጥኤም፤* ም47 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፍ10፥14 ማብ ይመ። *አስቀሎና፣ ጋዛ፣ አቃሮን፤* የመሳ1፥18 ማብ ይመ። *በአዛጦንም ሕዝብ ቅሬታ፤* ግሪካዊው ታሪክ ጸሓፊ ሄሮዶቱስ በዘገበው መሠረት፣ አዛጦን (አሽዶድ) የግብፅ ንጉሥ ረጅም ጦርነት ካካሄደበት በኋላ በግብፅ እጅ ወደቀች፤ እንዳልነበረችም ሆና ነበር፤ በነህምያ ዘመን ግን ነዋሪዎች እንደ ገና ሰፈሩባት (የነህ4፥7 ማብ ይመ)።

*25፥21-22፤* 27፥3-5 ይመ።

25፥21 *ኤዶምን፤* 49፥7-22 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፍ 36፥1 ማብ ይመ። *ሞዓብን፣ አሞንን፤* 48፥1-49፥6 ይመ፤ በተጨ ማሪም የዘፍ19፥36-38 ማብ ይመ።

*25፥22፤ የጢሮስንና ሲዶናን፤* 47፥4 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ23፥1-2:4:12 ማብ ይመ። *ከባሕሩ ማዶ ያሉ የጠረፍ ምድር፤* ደሴቶች ባሕር ገጠም የሆኑ አካባቢዎች ነበሩ፤ አንዳን ዶቹም ከጢሮስና ሲዶና የወደብ ከተሞች በስተ ምዕራብና በስተ ሰሜን ምዕራብ ይገኙ የነበሩ የፊንቂያውያን ቅኝ ግዛት የነበሩ ቦታዎች ናቸው (የሕዝ27፥15፤ የዳን11፥18 ማብ ይመ)።

25፥23 *ድዳንን፤* 49፥8 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ21፥13፤ የሕዝ25፥13 ማብ ይመ። *ቴማንን፤* የኢሳ21፥14 ማብ ይመ። *ቡዝን፤* ወደ ምሥራቅ አካባቢ የሚገኝ በረሓማ ቦታ ነበር። *ጠጕ ራቸውን ዙሪያውን የሚከረከሙትን ሕዝብ፤* ይህን አባባል አንዳንዶቹ፣ "ከሩቅ ስፍራ ያለ ሕዝብ" ብለው ይተረጕሙታል፤ የ9፥26 ማብ ይመ።

25፥24 *ዐረብ፤* 49፥28-33 ይመ፤ በተጨማሪም 3፥2 ይመ። *ድብልቅ ሕዝብ፤* ቍ20፤ ነህ13፥3 ይመ፤ አንዳንዶች ይህንኑ፣ "መጻተኞች" ብለው ይተረጕማሉ፤ በዕብራይስጡ ለዚህ የገባው ቃል "ዐረብ" እንዲሁም "መጻተኛ" ከሚሉት ቃላት ጋር የጋራ ሥርወ ቃል አላቸው።

25፥25 *የዘምሪ፤* ይህ ስም ከእስራኤላዊው ንጉሥ ስም ጋር እንደ አንድ መቈጠር የለበትም። ዘምሪ የሚለው ቃል ምናልባት ኬጡራ ለአብርሃም ከወለደችለት ሰው ስም ጋር አንድ ሳይሆን አይቀርም (የዘፍ25፥1-2 ይመ)። ዘምሪ የተባለው የት እንደ ሆነ በውል ያልታወቀው ይህ ስፍራ ስሙን ያገኘው ከዛምሪ ሳይሆን አይቀርም። *የኤላምና፤* 49፥34-39 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፍ 10፥22 ማብ ይመ። *የሜዶን፤* ይህ መንግሥት የኋላ ኋላ ባቢ ሎንን ለመውጋት ከፋርስ መንግሥት ጋር አበረ (51፥11:28 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሳ13፥17 ማብ ይመ)።

*25፥26፤ የሺሻክ፤* የባቢሎን ምስጢራዊ መጠሪያ ነው። *ይጠጣል፤* እግዚአብሔር ዓላማውን የሚፈጽምበት መሣሪያ የሆነ ሰው ወይም መንግሥት ራሱ ካመፀ፣ በጊዜው ከመቀጣት አያመ ልጥም (51፥48-49 ይመ)።

25፥27 *በምሰደው ሰይፍ ፊት ውደቁ፤* የቍ16 ማብ ይመ።

25፥29 *እጀምራለሁ፤* የቍ18 ማብ ይመ። *ስሜ የተጠራ በትን ከተማ፤* ኢየሩሳሌምን ማለት ነው (የ7፥10 ማብ ይመ)።

25፥30 *እግዚአብሔር ከላይ ይጮኻል ... ነጐድጓዳማ ድምፁን ያሰማል፤* የኢል3፥16፤ የአሞ1፥2 ሐሳብ እዚህ ላይ ይን ጸባረቃል (ያንኑ ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ሆሴ11፥10፤ አሞ3፥8 ይመ)። *በራሱ ምድር፤* የይሁዳን አገር ማለት ነው። *እንደ ወይን ጨማቂዎች ... ያስገመግማል፤* ኢሳ9፥3፤ 16፥9-10፤ 63፥3 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ16፥10 እና ማብ ይመ።

25፥31 *ታላቅ ጩኸት፤* በጦርነት ጊዜ የሚሰማውን የውካታ ድምፅ ለመግለጽ የገባ ነው (አሞ2፥2 ይመ)። *ይፋረ ዳልና ... ፍርድን ያመጣል፤* የ2፥9 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 2፥35፤ 12፥1 ይመ።

25፥32 *ብርቱ ዐውሎ ነፋስ ከምድር ዳርቻ፤* የእግዚአ ብሔር ቍጣ (23፥19 ይመ) በባቢሎናውያን ወረራ አማካይነት

ከምድር ዳርቻ ተነሥቶአል።

33በዚያን ጊዜ *በእግዚአብሔር* የተገደሉት ከምድር ዳር እስከ ምድር ዳር በሁሉ ስፍራ ተረፍርፈው ይታያሉ፤ እንደ ጕድፍ በምድር ላይ ይጣላሉ እንጂ፣ አይለቀስላቸውም፤ ሬሳ ቸውም አይሰበሰብም፤ አይቀበርምም።

34እናንት እረኞች፤ አልቅሱ፤ ዋይ በሉ፤
እናንት የመንጋው ጌቶች፤ በዐመድ ላይ
ተንከባለሉ፤
የምትታረዱበት ቀን ደርሶአልና፤
እንደ ውብ የሸክላ ዕቃ ወድቃችሁ
ትከሰክሳላችሁ።
35እረኞች የሚሸሹበት፣
የመንጋ ጠባቂዎችም የሚያመልጡበት
የለም።
36*እግዚአብሔር* ማሰማሪያቸውን
አጥፍቶአልና፣
የእረኞችን ጩኸት፣
የመንጋ ጠባቂዎችን ዋይታ ስሙ።
37*ከእግዚአብሔር* ጽኑ ቍጣ የተነሣ፣
ሰላማዊው ምድር ባድማ ይሆናል።
38እንደ አንበሳ ከጕሬው ይወጣል፤
ከአስጨናቂው ሰይፍ፣[1]
ከቍጣውም የተነሣ፣
ምድራቸው ባድማ ትሆናለች።

## በኤርምያስ ላይ የግድያ ዛቻ

**26** በይሁዳ ንጉሥ፣ በኢዮስያስ ልጅ፣ በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ ይህ ቃል *ከእግዚአብሔር* ዘንድ መጣ፤ 2"*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ *በእግዚአብሔር* ቤት አደባባይ ቆመህ፣ ለማ ምለክ ወደ *እግዚአብሔር* ቤት ከይሁዳ ከተሞች ለሚመጣው ሕዝብ ሁሉ ተናገር፤ አንዲትም ቃል ሳታስቀር የማዝህን ሁሉ ንገራቸው። 3ምናልባትም ሰምተው እያንዳን ዳቸው ከክፉ መንገዳቸው ይመለሱ ይሆናል፤ እኔም ስላደረጉት ክፋት ላመጣባቸው ያሰ ብሁትን ቅጣት እተዋለሁ። 4እንዲህም በላቸው፤ '*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ባትሰሙኝና የሰጠኋችሁን ሕጌን ባትጠ ብቁ፣ 5ልትሰሟቸው ይገባ የነበረውን ወደ እናንተ ደጋግሜ የላክኋቸውን የአገል ጋዮቼን የነቢያትን ቃል ባትሰሙ፣ 6ይህን ቤት እንደ ሴሎ አደርጋለሁ፤ ይህችንም ከተማ በምድር ሕዝብ ሁሉ ፊት የተረገ መች አደርጋታለሁ።' "

7ኤርምያስ ይህን ቃል *በእግዚአብሔር* ቤት ሲናገር፣ ካህናቱና ነቢያቱ፣ ሕዝቡም ሁሉ ሰሙ። 8ነገር ግን ኤርምያስ *እግዚ አብሔር* ለሕዝቡ ሁሉ እንዲናገር ያዘዘውን ሁሉ ተናግሮ በጨረሰ ጊዜ፣ ካህናቱ፣ ነቢ ያቱና ሕዝቡም ሁሉ ይዘውት እንዲህ አሉ፤ "አንተ መገደል አለብህ! 9ይህ ቤት እንደ ሴሎ ይሆናል፤ ይህቺም ከተማ ባድማና ወና ትሆናለች ብለህ *በእግዚአብሔር* ስም ለምን ትንቢት ትናገራለህ?" ' ሕዝቡም ሁሉ *በእግዚአብሔር* ቤት ውስጥ ተሰብስ በው ኤርምያስን ከበቡት።

10የይሁዳም ባለሥልጣኖች ስለ እነዚህ ነገሮች በሰሙ ጊዜ፣ ከቤተ መንግሥት ወደ *እግዚአብሔር* ቤት ወጡ፤ *በእግዚ አብሔር* ቤት፣ 'አዲሱ በር' በተባለው መግቢያ ተቀመጡ። 11ካህናቱና ነቢያቱም ለባለሥልጣኖቹና ለሕዝቡ ሁሉ፣ "በጆሮአ ችሁ እንደ ሰማችሁት ይህ ሰው በዚህች

[1]38 አንዳንድ የዕብራይስጥና የሰብዓ ሊቃናት ትርጕሞች (ኤር46፥16 እና 50፥16 ይመ) *ቍጣ* ይላሉ

25፥33 መዝ79፥3፤ ኢሳ66፥16፤ኤር8፥2 ፤ሕዝ39፥17-20
25፥34 መዝ44፥22 ፤ኢሳ34፥6፤ኤር2፥8፤ 6፥26፤22፥28፤50፥27 ፤51፥40፥ዘካ10፥3፤ 11፥4:7
25፥35 ኢዮ11፥20
25፥36 ኤር6፥26፤ 23፥1፤ዘካ11፥3
25፥38 ዘፀ15፥7፤ ኢዮ10፥16፤ኤር4፥7 :26፤44፥22፤46፥16፤ 50፥16
26፥1 2ነገ23፥36
26፥2 ቍ12፤ዘዳ 4፥2፤ኤር1፥17፤17፥ 19፤19፥14፤ማቴ 28፥20፤ሐሥ20፥27
26፥3 ዘዳ30፥2፤ 2ዜና33፥12-13፤ኢሳ 55፥7፤ኤር18፥8፤35፥ 15፤36፥7
26፥4 ዘፀ20፥1-23፥ 33፤ዘሌ26፥14፤1ነገ 9፥6፤ኤር11፥8፤25፥3
26፥5 ምሳ1፥24፤ ኢሳ65፥12፤ኤር25፥4 ፤44፥5
26፥6 ዘዳ28፥25፤ ኢሱ18፥1፤መሳ18፥31 ፤2ነገ22፥19
26፥8 ዘሌ24፥15-16 ፤ነህ9፥26፤ኤር11፥21፤ 43፥1፤ሐሥ6፥12፤ 21፥27
26፥9 ዘሌ26፥32፤ኤ ር9፥11፤ሐሥ21፥32
26፥10 ቍ16፤ዘፍ 23፥10፤ኤር34፥19፤ ሕዝ22፥27
26፥11 ዘዳ18፥20፤ መዝ44፥1፤ኤር11፥21 ፤18፥23፤ማቴ26፥66፤ ሐሥ6፥11

ወደ ይሁዳ ምድር መፋጠኑን የሚያመለክት ነው (የኢሳ41፥25 ማብ ይመ)።

25፥33 *እንደ ጕድፍ በምድር ላይ ይጣላሉ ... አይለቀስ ላቸውም*፤ ከ8፥2 የተደገመ ሐሳብ ነው (ያንኑ ማብ ይመ)፤ በ16፥4 ላይ ይህ ቃል አለ።

25፥34-36 እረኞች ... የመንጋው ጌቶች፤ 10፥21፤ 22፥22 ይመ።

25፥34 *በዐመድ ላይ ተንከባለሉ*፤ "በዐፈር ላይ ተንከባ ለሉ" የሚሉ ትርጕሞች አሉ (6፥26 ይመ)። *ቀን ደርሶአልና (የምትታረዱበት)*፤ ሰ.ኤር4፥18 ይመ። *እንደ ውብ የሸ ክላ ዕቃ ... ትከሰከሳላችሁ*፤ በ22፥28 ላይ ስለ ንጉሡ ስለ ኢኮን ያን ከተነገረው ጋር ያነጻጽሩ።

*26፥1-24*፤ ኤርምያስ በም7 ላይ፣ በቤተ መቅደስ አደባ ባይ ካስተላለፋቸው መልእክቶች ውስጥ (የ7፥1-10-25 ማብ ይመ)፣ የአንዱ መልእክት አጭር መግለጫና (ቍ4-6) ውጤቱ (ቍ7-24) በዚህ ክፍል ቀርቦአል።

26፥1 *ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ*፤ 27፥1 ይመ፤ ዘመኑ 609-608 ዓ.ቅ.ክ እንደ ሆነ ይገመታል።

26፥2 *በእግዚአብሔር ቤት አደባባይ*፤ 'አዲሱ በር' በተባ ለው መግቢያ (ቍ10 ይመ፤ በተጨማሪም የ7፥2 ማብ ይመ) አጠገብ ሳይሆን አይቀርም። *ለማምለክ ... ለሚመጣው*፤ 7፥2 እና ማብ ይመ። *አንዲትም ቃል ሳታስቀር*፤ ዘዳ4፥2 እና ማብ ይመ። ኤርምያስ ሰዎቹን ስለ ፈራ እግዚአብሔር ከነገረው አንዳንዱን መራር ቃል ለማስቀረት ተፈትኖ፣ ሁለት ልብ የመ ሆን ሁኔታ ሳያጋጥመው አልቀረም።

*26፥3*፤ 7፥3:5-7 ይመ። *ይመለሱ ይሆናል*፤ ቍ13:19 ይመ፤ በተጨማሪም የ4፥28፤ የ18፥7-10 ማብ ይመ።

26፥4 *ባትሰሙኝና*፤ ቍ5፤ 7፥13 ይመ። *ሕጌን*፤ 7፥6:9 እና ማብ ይመ።

*26፥5*፤ 7፥13:25-26 ይመ። *የአገልጋዮቼን የነቢያትን*፤ የ7፥25 ማብ ይመ። *ደጋግሜ*፤ የ7፥13 ማብ ይመ።

26፥6 *ይህን ቤት እንደ ሴሎ አደርጋለሁ*፤ ቍ9 ይመ፤ በተጨማሪም የ7፥12 ማብ ይመ። *ይህችንም ከተማ*፤ ኢየሩ ሳሌምን ነው። *የተረገመች*፤ 24፥9፤ 25፥18 ይመ፤ በተጨማሪም የዘካ8፥13 ማብ ይመ።

26፥8 *አንተ መገደል አለብህ*፤ በዘፍ2፥17 ላይ ተመሳሳዩ የዕብራይስጥ ሐረግ፣ "ሞትን ትሞታለህ" ተብሎ ተተርጕሞአል። ወደዚህኛው ሐረግ በጣም የሚቀርበው ተመሳሳይ ሐረግ፣ የሙ ሴን ሕግ በተላለፈ ሰው ላይ የሚደርሰውን የመጨረሻ ቅጣት ይገልጻል (ለምሳሌ:- ዘፀ21፥15-17፤ ዘሌ24፥16-17:21፤ ዘዳ18፥20 ይመ፤ ከ1ነገ 21፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

26፥9 *ከበቡት*፤ ለበጎ ሳይሆን ክፉ ዐላማ በመያዝ ነው (ዘኍ16፥3 ይመ)።

26፥10 *የይሁዳም ባለሥልጣኖች*፤ በቤተ መቅደስ አካባቢ ለሚነሣ ለማንኛውም ክርክር ሕጋዊ መፍትሔ የመስጠት ኀላፊነት አለባቸው። ካህናቱና ሐሰተኞቹ ነቢያት ኢየሩሳሌምንና ቤተ መቅደሷን ከጥቅም አንጻር በተለየ ዐይን ስለሚመለከቱት፣ ኤርምያስ ስለ ከተማዋና ስለ እግዚአብሔር ቤት መጥፋት ትን ቢት እየተናገረ ስለ ነበር፣ የሞት ፍርድ እንደሚገባው ገለጹ (ቍ8-9:11 ይመ)። ሆኖም ኤርምያስ የመከላከያ መልሱን ባቀረበ ጊዜ ነገሩን ሰምተው ካመዛዘኑ በኋላ (ቍ12-15)፣ እርሱን የሚደግፍ ውሳኔ አስተላለፉ (ቍ16)። ሕዝቡም በወላዋይ አቋ ማቸው በመጀመሪያ ኤርምያስን ተቃውመው ነበር (ቍ8-9)፤ ይደግፉትም ጀመር (ቍ16)። *'አዲሱ በር'*፤ 36፥10 ይመ፤ ምናልባት፣ 'የላይኛው የብንያም በር' ከተባለው ጋር (20፥2 እና ማብ ይመ) አንድ ሳይሆን አይቀርም።

*26፥11*፤ እዚህ ላይ የኤርምያስ ጠላቶች የመከላከያ መልስ

ከተማ ላይ ትንቢት ስለ ተናገረ ሞት ይገባዋል" አሉ።

[12]ኤርምያስም፣ ለባለሥልጣኖቹና ለሕዝቡ ሁሉ እንዲህ አለ፤ "የሰማችሁትን ሁሉ በዚህ ቤትና በዚህች ከተማ ላይ ትንቢት እንድናገር *እግዚአብሔር* ልኮኛል። [13]አሁንም መንገዳችሁንና ሥራችሁን አስተካክሉ፣ ለአምላካችሁን *እግዚአብሔርን* ታዘዙ። *እግዚአብሔርም* በእናንተ ላይ ለማምጣት የተናገረውን ክፉ ነገር ይተዋል። [14]ስለ እኔ ከሆነ ግን እነሆ፤ በእጃችሁ ነኝ፤ መልካምና ተገቢ መስሎ የሚታያችሁን ሁሉ አድርጉብኝ። [15]ነገር ግን የሰማችሁትን ይህን ሁሉ ቃል በጆሮአችሁ እንድናገር *እግዚአብሔር* በእርግጥ ስለ ላከኝ ብትገድሉኝ፣ የንጹሕ ሰው ደም በማፍሰሳችሁ እናንተ ራሳችሁንና ይህቺን ከተማ፣ በውስጧም የሚኖረውን በደለኛ እንዳታደርጉ ተጠንቀቁ።"

[16]ባለሥልጣኖቹና ሕዝቡም ሁሉ ለካህናትና ለነቢያት፣ "ይህ ሰው በአምላካችን *በእግዚአብሔር* ስም ተናግሮአልና ሊገደል አይገባውም" አሉ።

[17]ከአገሩ ሽማግሌዎችም አንዳንዶቹ ተነሥተው ለተሰበሰበው ሕዝብ ሁሉ እንዲህ አሉ፤ [18]"ሞሬታዊው ሚክያስ በይሁዳ ንጉሥ በሕዝቅያስ ዘመን፣ ለይሁዳም ሕዝብ ሁሉ እንዲህ ሲል ትንቢት ተናግሮ ነበር፤ 'የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

" 'ጽዮን እንደ እርሻ ትታረሳለች፤
ኢየሩሳሌም የፍርስራሽ ክምር ትሆናለች፤
የቤተ መቅደሱም ተራራ፣ ዳዋ የወረሰው ኮረብታ ይሆናል።'[ኀ]

[19]"ታዲያ፣ የይሁዳ ንጉሥ ሕዝቅያስም ሆነ የይሁዳ ሕዝብ ሁሉ ገደሉትን? ሕዝቅያስ *እግዚአብሔርን* ፈርቶ ምሕረት አልለመነምን?' *እግዚአብሔርስ* በእነርሱ ላይ ለማምጣት ያሰበውን ቅጣት አልተወምን? በራሳችን ላይ እኮ ታላቅ ጥፋት እያመጣን ነው።"

[20]ደግሞም የቂርያትይዓሪም ሰው፣ የሸማያ ልጅ ኦርዮ፣ *በእግዚአብሔር* ስም ትንቢት የተናገረ ሌላው ሰው ነበር፤ እርሱም እንደ ኤርምያስ በዚህች ከተማና በዚህ ምድር ላይ ትንቢት ተናግሮ ነበር። [21]ንጉሥ ኢዮአቄም፣ የጦር አለቆቹና ባለሥልጣኖቹ ሁሉ ይህን በሰሙ ጊዜ፣ ንጉሡ ሊገድለው ፈለገ፤ ኦርዮም ይህን ሰምቶ በፍርሀት ወደ ግብፅ ሸሸ። [22]ይሁን እንጂ ንጉሥ ኢዮአቄም የዓክቦርን ልጅ ኤልናታንንና ከእርሱም ጋር ሌሎችን ሰዎች ወደ ግብፅ ላካቸው፤ [23]እነርሱም ኦርዮን ከግብፅ አምጥተው፣ ወደ ንጉሥ ኢዮአቄም ወሰዱት፤ እርሱም በሰይፍ ገደለው፤ ሬሳውንም ተራ ሰዎች በሚቀበሩበት ስፍራ ጣለው።

[24]ነገር ግን የሳፋን ልጅ አኪቃም ከኤር

[ኀ]18 ሚክያስ 3፥12

26፥12 ቍ2:15፤ ኢሳ6፥8፤ኤር1፥18፤ አሞ7፥15፤ሐሥ4፥18-20፤5፥29
26፥13 ኤር7፥5፤ 11፥4፤18፥8፤ኢል 2፥12-14
26፥14 ኢሱ 9፥25፤ ኤር 38፥5
26፥15 ቍ12፤ዘዳ 19፥10፤ኤር1፥17
26፥16 ቍ10፤ሐሥ 23፥9:29
26፥18 2ነገ25፥9፤ ነሀ4፥2፤ኢሳ2፥3፤ኤር 9፥11፤17፥3፤ሚክ1፥1 ፤4፥1፤ዘካ 8፥3
26፥19 ዘፀ32፥14፤ 1ሳሙ13፥12፤1ዜና 3፥13፤2ዜና32፥24-26፤ኢሳ37፥14-20፤ ኤር18፥8፤44፥7፤ዕን 2፥10
26፥20 ኢሱ9፥17
26፥21 ቍ10፤ዘፍ 31፥21፤1ነገ19፥2፤ ኤር2፥30፤ማቴ 10፥23፤23፥37
26፥22 ኤር36፥12 ፡25
26፥23 2ነገ23፥6፤ ዕብ11፥37
26፥24 2ነገ22፥12

ለመስጠት ጊዜ ሳይሰጡት፣ ቶሎ ሲፈርዱበት ይታያሉ (ዘዳ19፥6 ይመ)።

26፥12 *እግዚአብሔር ልኮኛል፤* ከ23፥21 ጋር ያገናዝቡ።

26፥13 *መንገዳችሁንና ሥራችሁን አስተካክሉ፤* የ7፥3 አባባል እዚህ ላይ ተደግሞአል (በተጨማሪም 18፥11፤ 35፥15 ይመ)። *ይተዋል፤* ቍ3:19 ይመ። በተጨማሪም የ4፥28፤ የ18፥7-10 ማብ ይመ።

26፥15 *የንጹሕ ሰው ደም፤* 7፥6 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ማቴ27፥24-25፤ ሐሥ5፥28 ይመ።

*26፥16፤* ከቍ11 ጋር ያገናዝቡ፤ የቍ10 ማብ ይመ።

26፥17 *ሽማግሌዎችም፤* 19፥1 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፀ 3፥16 ማብ ይመ።

*26፥18-19፤* ሽማግሌዎቹ ከአንድ ምዕተ ዓመት በፊት የነበረውን ሚክያስን የታሪክ ማስረጃ አድርገው ይጠቅሱታል፤ እርሱና ኢሳይያስ በዘመናቸው የነበረውን ንጉሥ ሕዝቅያስን ስለ ሕዝቡ ምሕረት እየጠየቀ እንዲጸልይ አግባብተውት ነበር። እግዚአብሔርም የንጉሡንና የነቢዩን ጸሎት በመስማት በ701 ዓ.ቅ.ክ ኢየሩሳሌምንና ቤተ መቅደሱን ከጥፋት አድኖአል (ኢሳ 37፥33-37 ይመ)።

26፥18 *ሞሬታዊው ሚክያስ፤* የነቢዩ የሚክያስ የትውልድ ከተማ ሞሬት ወይም ሞሬሼትጌት በደቡብ ይሁዳ ትገኝ ነበር (ሚክ1፥1:14 ይመ)። *ጽዮን ... ትታረሳለች ... ዳዋ የወረሰው ... ይሆናል፤* ከሚክ3፥12 ቃል በቃል የተጠቀሰ ነው፤ በብሉይ ኪዳን ውስጥ አንድ ነቢይ ከሌላው በመጥቀስ ሲጽፍና ከየት እንደ ተጠቀሰም በግልጽ ሲያስቀምጥ የታየው በእዚህ ክፍል ነው።

26፥19 *ምሕረትን አልለመነምን?* የዕብራይስጡ ሐረግ ቃል በቃል ሲተረጐም "ፊቱን አልዳሰስንምን?" የሚል ነው (ከመዝ119፥58 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ወይም "ጒንጩን አልዳበስንምን" ማለት ይሆናል (ዘፀ32፥11፤ 1ሳሙ13፥12፤ 2ነገ13፥4 ይመ)። *አልተወምን?* ቍ3:13 ይመ፤ በተጨማሪም የ4፥28፤ የ18፥7-10 ማብ ይመ።

*26፥20-23፤* በዚህ ክፍል ያለው ታሪክ የገባው፣ መልካሙ ንጉሥ ሕዝቅያስ የጌታን ነቢያት እንዴት በበጎነት እንደ ተንከባከባቸውና ክፉው ንጉሥ ኢዮአቄም ግን ምን ያህል ችግር እንዳደረሰባቸው በማነጻጸር ለማሳየት ብቻ እንጂ፣ የታሪኩ ሂደት ከኤርምያስ ዘመን ጋር ግንኙነት ኖሮት አይደለም።

26፥20 *ኦርዮ፤* ይህ ሰው ከብሉይ ኪዳን ውስጥ በየትኛውም ስፍራ ስሙ ተጠቅሶ አይገኝም፤ ይሁን እንጂ "የለኪሶ መልእክቶች" በተባለው የጽሑፍ ግኝት ውስጥ እንደ ተጠቀሰ ይነገራል (የ34፥7 ማብ ይመ)።

26፥21 *የጦር አለቆቹና፤* ዕብራይስጡ፣ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ኀያላን ሰዎች" የሚል ነው (ምናልባት የክብር ዘበኞች ሳይሆኑ አይቀሩም)። *ኦርዮም ... ወደ ግብፅ ሸሸ፤* ሸሽቶ ማድረጉ ትልቅ ስሕተት ነበር፤ ምክንያቱም አገር ጥሎ መሄድ ራሱ ከክሕደትና ዐመፅን ከማነሣሣት ይቈጠራል፤ ሊሞት የበቃውም ይህ ስለ ተጨመረበት ሳይሆን አይቀርም።

26፥22 *የዓክቦርን ልጅ ኤልናታንንና፤* ከንጉሥ ኢዮአቄም ከፍተኛ ባለሥልጣኖች አንዱ ነበር (36፥12 ይመ)፤ በሌላ ጊዜ ኤርምያስ በሚናገረው ትንቢት ልቡ ተነክቶ ነበር (36፥16 ይመ)፤ ንጉሡ የኤርምያስን የብራና መጽሐፍ እንዳያቃጥል ለምነው (36፥25)፤ ነቢዩም እንዲደበቅ አስጠነቀቀው (36፥19)። ኤልናታን (ምናልባትም ይህኛው ሊሆን ይችላል) የተባለ ሰው የኢዮአቄም አማት ነበር (2ነገ24፥6:8 ይመ)። ዓክቦር የተባለው ሰው ደግሞ (የዚሁ የኤልናታን አባት ሊሆን ይችላል) ከንጉሥ ኢዮስያስ ባለሥልጣኖች አንዱ ነበር (2ነገ22፥12:14 ይመ፤ በተጨማሪም የቍ24 ማብ ይመ)።

26፥23 *ኦርዮን ከግብፅ አምጥተው፤* ኢዮአቄም የዳግማዊው ፈርዖን ኒካዑ አገልጋይ እንዲሆን በተወሰነ ጊዜ 2ነገ 23፥34-35 ይመ)፣ ግብፅ በይሁዳ ላይ ከጣለችው ግዴታ አንዱ እስረኛ የመለዋወጥ ስምምነት ነበር። *ኢዮአቄም ... በሰይፍ ገደለው፤* ኤርምያስም የእግዚአብሔር ጥበቃ ባይበዛለት ኖሮ፣ ተመሳሳይ ዕድል በገጠመው ነበር (36፥26 ይመ። *ተራ ሰዎች በሚቀበሩበት ስፍራ፤* የ17፥19 ማብ ይመ። ተራ ሰዎች ሲሞቱ የሚቀበሩት፣ ከኢየሩሳሌም በስተ ምሥራቅ በሚገኘው በቄድሮን ሸለቆ ውስጥ ነበር (2ነገ23፥6 ይመ)።

26፥24 *የሳፋን ልጅ አኪቃም፤* ከንጉሥ ኢዮስያስ ባለሥልጣኖች አንዱ ነበር (2ነገ22፥12:14 ይመ)፤ በቍ22 ላይ የኤልናታን አባት ይሆናል ከሚባለው ከዓክቦር ጋር አብረው

ምያስ ጕን ስለ ቆመ፣ ኤርምያስ ይገደል ዘንድ ለሕዝቡ ዐልፎ አልተሰጠም።

## የይሁዳ በናቡከደነፆር ሥር መውደቅ

**27** በይሁዳ ንጉሥ፣ በኢዮስያስ ልጅ በሴዴቅያስ[a] ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ ይህ የእግዚአብሔር ቃል ወደ ኤርምያስ መጣ፤ [2]እግዚአብሔርም እንዲህ አለኝ፤ "የዕንጨት ቀንበር ሠርተህ በጠፍር ማነቆ አያይዘውና በዐንገትህ አስገባው፤ [3]ወደ ይሁዳ ንጉሥ ወደ ሴዴቅያስ ወደ ኢየሩሳሌም በመጡት ሰዎች በኩል ለኤዶም፣ ለሞዓብ፣ ለአሞን፣ ለጢሮስና ለሲዶና ነገሥታት መልእክት ላክ። [4]ለጌቶቻቸውም እንዲያሳውቁ እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ 'የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ለጌቶቻችሁ ይህን ንገሯቸው፤ [5]በታላቁ ኀይሌና በተዘረጋው ክንዴ ምድርን፣ በላይዋ የሚኖሩትን ሰዎችና እንስሳት ፈጥሬአለሁ፤ ለምወደውም እሰጣለሁ። [6]አሁንም እነዚህን አገሮች ሁሉ ለአገልጋዬ ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደነፆር አሳልፌ እሰጣለሁ፤ የዱር አራዊት እንኳ እንዲገዙለት አደርጋለሁ። [7]የእርሱ አገር በተራው ለሌሎች እስከሚገዛበት ጊዜ ድረስ፣ ሕዝቦች ሁሉ ለእርሱ፣ ለልጁና ለልጅ ልጁ ይገዛሉ፤ በዚያን ጊዜ ብዙ ሕዝቦችና ታላላቅ ነገሥታት እርሱን ይገዙታል።

[8]" ' "ነገር ግን ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደናፆር የማይገዛ፣ ዐንገቱንም ከቀንበሩ በታች ዝቅ የማያደርግ ማንኛውንም ሕዝብ ወይም መንግሥት በእጁ እስከማጠፋው ድረስ በሰይፍና በራብ፣ በመቅሠፍትም እቀጣዋለሁ፤ ይላል እግዚአብሔር፤ [9]ስለዚህ፣ 'የባቢሎንን ንጉሥ አታገለግሉም' የሚሏችሁን ነቢያታችሁን፣ ሟርተኞቻችሁን፣ ሕልመኞቻችሁን፣ መናፍስት ጠሪዎቻችሁንና መተተኞቻችሁን አትስሙ፤ [10]ከምድራችሁ እንድትፈናቀሉ፣ እኔም እንዳሳድዳችሁና እንዳጠፋችሁ የሐሰት ትንቢት ይነግሯችኋልና። [11]ነገር ግን ከባቢሎን ንጉሥ ቀንበር በታች ዐንገቱን ዝቅ የሚያደርገውንና የሚያገለግለውን ማንኛውንም ሕዝብ በገዛ ምድሩ እንዲቀርና እያረሰም በዚያ እንዲኖር አደርገዋለሁ፤ ይላል እግዚአብሔር።" ' "

[12]ለይሁዳ ንጉሥ ለሴዴቅያስም ይህንኑ መልእክት እንዲህ ብዬ ነገርሁት፤ "ዐንገታችሁን ከባቢሎን ንጉሥ ቀንበር በታች ዝቅ አድርጉ፤ እርሱንና ሕዝቡን አገልግሉ፤ በሕይወትም ትኖራላችሁ። [13]አንተና ሕዝብህ፣ እግዚአብሔር ለባቢሎን ንጉሥ አልገዛም ያለውን ሕዝብ ባስጠነቀቀበት በሰ

27፥1 2ዜና36፥11
27፥2 ዘሌ26፥13፤ 1ነገ22፥11
27፥3 ዘፍ10፥15፤ ኤር25፥17፡21፡22
27፥5 ዘፍ1፥1፡25፤ ዘዳ9፥29፤መዝ115፥16፤ ዳን4፥17
27፥6 ኤር21፥7፤ 25፥9፤28፥14፤ዳን 2፥37-38
27፥7 2ዜና36፥20፤ ኤር25፥12፡14፤ 51፥47፤ዳን5፥18፡28
27፥8 ኤር5፥12፤ 9፥16፤14፥12፤21፥9
27፥9 ዘፀ30፥27፤ ዘፀ7፥11፤ዘዳ13፥1፤ 18፥11፤ኢሳ44፥25፤ ኤር6፥14፤23፥25፤ ሕዝ13፥1-23
27፥10 2ነገ23፥27፤ ኤር23፥25፤ማር13፥5
27፥11 ዘዳ6፥2፤ኤር 21፥9
27፥12 ኤር17፥4፤ 21፥9
27፥13 ኤር14፥12፤ ሕዝ18፥31

[a]1 ጥቂት የዕብራይስጥ ጽሑፎችና የሱርስት ትርጕም (ኤር 27፥3፡12 እና 28፥1 ይመ)፣ አንዳንድ የዕብራይስጥ ጽሑፎች ኢዮአቄም ይላሉ (አብዛኛዎቹ የሰብዓ ሊቃናት ትርጕሞች ይህ ጥቅስ/ ቍጥር የላቸውም)።

ባለሥልጣን ነበሩ (የቍ22 ማብ ይመ)። *አኪቃም፤* ኢየሩሳሌም በ586 ዓ.ቅ.ክ ከወደመች በኋላ፣ የይሁዳ ገዥ የሆነው የጎዶልያስ አባት ነበር (40፥5 ይመ)፤ ጎዶልያስ ለኤርምያስ ጥሩ ወዳጅ ሆኖ ነበር (39፥14 ይመ)። *ከኤርምያስ ጐን ስለ ቆመ፤* አኪቃም በኢዮአቄም መንግሥት ውስጥ ታላቅ ስፍራ የነበረው ሰው በመሆኑ፣ የነቢዩን ሕይወት በማትረፍ ረገድ ትልቅ ሚና መጫወቱ አያጠራጥርም።

*27፥1-29፥32፤* ኤርምያስ እዚህ ላይ 'የባቢሎን ውድቀት ተቃርቦአል፤ ስለዚህ በናቡከደነፆር ላይ ማመፅ አስፈላጊ ነው፤ ችግርም አያስከትልም' በማለት የሚያስተምሩትን ሐሰተኞች ነቢያት እንደ ገና ለመቋቋም ሲሞክር ይታያል።

*27፥1-22፤* ኤርምያስ ሕዝቡ (ቍ3-11 ይመ)፣ ንጉሥ ሴዴቅያስ (ቍ12-15 ይመ) እንዲሁም ካህናቱና የይሁዳ ሕዝብ (ቍ16-22 ይመ) ምርኮኛ ሆነው በባቢሎን ይገዙ ዘንድ ፈቃደኞች እንዲሆኑ ይነግራቸዋል።

27፥1 *ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ፤* የ26፥1 ማብ ይመ። በዚህኛው ላይ ግን የሐረጉን ትርጕም ሰፋ በማድረግ አራተኛውን የሴዴቅያስን የንግሥና ዘመን እንዲያካትት ተደርጎአል (593 ዓ.ቅ.ክ፤ 28፥1 ይመ)።

27፥2 *ቀንበር፤* በሬዎች ለዕርሻ ሥራ የሚጠመዱበት መሣሪያ ሲሆን፣ በፖለቲካዊ አገባቡ የመገዛትና እጅ የመስጠት ምልክት ነው (ቍ8፡11-12፤ ዘሌ26፥13 ይመ)። ኤርምያስ በእርግጥ ቀንበር አንገቱ ላይ አስገብቶ ጥቂት ጊዜ እንደ ተመላለሰ፣ ከ28፥10፡12 በግልጽ ማወቅ ይቻላል።

27፥3 *መልእክት ላክ፤* "ለሕዝቦች ነቢይ" በመሆኑና በነበረው ኀላፊነት (1፥5)። *ለኤዶም፣ ለሞዓብ፣ ለአሞን፤* ከይሁዳ ምድር በስተ ምሥራቅና በስተ ደቡብ የሚገኙ አገሮች ነበሩ (25፥21 እና ማብ ይመ)። *ለጢሮስና ለሲዶና፤* ከይሁዳ በስተ ሰሜን በፊንቄ ምድር የታወቁ ሁለት ከተሞች (25፥22 እና ማብ ይመ)። *ወደ ሴዴቅያስ ... በመጡት ሰዎች፤* ምናልባት በባቢሎን ላይ ዐመፅ ለማካሄድ ንግግርና ምክክር ለማድረግ የመጡ ሳይሆኑ አልቀሩም። ከግብፅም ርዳታ እናገኛለን ብለው ሳይተማመኑ የቀሩ አይመስልም። ሴዴቅያስ ወደ ባቢሎን በ 593 ዓ.ቅ.ክ ሄዶአል (51፥59 ይመ)፤ ምናልባትም ናቡከደነፆር ሊጠይቀው የሚፈልገው ሳይኖር አልቀረም። ሆኖም ቀረም ሴዴቅያስ ዐምፆበታል (52፥3 ይመ)።

27፥5 *በታላቁ ኀይሌና በተዘረጋው ክንዴ፤* የ21፥5 ማብ ይመ።

27፥6 *ለአገልጋዬ ... ለናቡከደነፆር፤* የ25፥9 ማብ ይመ። *የዱር አራዊት ... እንዲገዙለት አደርጋለሁ፤* ለናቡከደነፆር የማይገዛ አይኖርም፤ ከሥልጣኑ ውጭ የሚሆን አይገኝም ማለት ነው (28፥14፤ ዳን2፥38 ይመ)።

27፥7 *ለእርሱ፣ ለልጁና ለልጅ ልጁ፤* ቀጥታ ከአባት ወደ ልጅ እየተላለፈ የሚሄድ ብቻ ሳይሆን፣ የሦስት ነገሥታትን ትውልዶች የሚያመለክት ነው (ከዘዳ6፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። በብሉይ ኪዳን ውስጥ ብዙውን ጊዜ "ልጅ"እና "አባት" በዘይቤአዊ አነጋገር ጥቅም ላይ ውሎ ይገኛል (የዳን5፥1 ማብ ይመ፤ "ልጅ" ሲባል፣ "ዘር" ማለት ይሆናል፤ "አባት" ሲባል ደግሞ፣ "የነገድ አባት" ወይም "የጐሣ መሥራች" ማለት ይሆናል)። *የእርሱ አገር ... እስከሚገዛበት ጊዜ ድረስ፤* የባቢሎን ምድርም ጊዜዋን ጠብቃ ፍርድ ትቀበላለች (የ25፥26 ማብ ይመ)። *ብዙ ሕዝቦችና ታላላቅ ነገሥታት፤* የ25፥14 ማብ ይመ።

27፥8 *ከቀንበሩ፤* የቍ2 ማብ ይመ። *በሰይፍ፣ በራብ፣ በመቅሠፍት፤* የ14፥12 ማብ ይመ። *እስከማጠፋው ድረስ* 9፥15፤ 24፥10 ይመ።

*27፥9፤* 29፥8 ይመ። *ነቢያታችሁን፤* ሐሰተኞቹን ነቢያት ነው። *ሟርተኞቻችሁን ... መናፍስት ጠሪዎቻችሁንና መተተኞቻችሁን፤* እንደነዚህ ያሉ ነገሮችን በእስራኤል ሕዝብ መካከል እንዳያደርጉ ተከልክለው ነበር (ዘሌ 19፥26፤ ዘዳ 18፥10-11 ይመ)። *ሕልመኞቻችሁን፤* ነቢያት ነን ባዮችንና ሟርተኞችን ሁሉ የሚያጠቃልል ነው (23፥25-28፤ 29፥8 ይመ)።

27፥10 *የሐሰት ትንቢት ይነግሯችኋልና፤* የ5፥31 ማብ ይመ፤ ከ2ጢሞ4፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ።

27፥11 *ቀንበር፤* የቍ2 ማብ ይመ። *የሚያገለግለውን ... እያረሰም፤* በዕብራይስጡ እነዚህ ሁለቱ ቃላት የተገኙት ከአንድ ሥርወ ቃል ነው (በማገልገልም፣ በማረስም "ሥራ" የተባለውን ቃል እኩል ይጋሩታል)።

27፥12 *አንገታችሁን ... አገልግሉ፤ በሕይወትም ትኖራላችሁ፤* በዕብራይስጥ በብዙ ቍጥር ተገልጦአል፤ ኤርምያስ የሚናገረው ለይሁዳ ሕዝብና ለንጉሥ ሴዴቅያስ ነውና (ቍ13 ይመ)።

ይፍ፣ በራብና በመቅሠፍት ለምን ታልቃላችሁ? [14]ሐሰተኛ ትንቢት ስለሚነግሯችሁ፣ 'የባቢሎንን ንጉሥ አታገለግሉም' የሚሏችሁን ነቢያት አትስሙ፤ [15]'እኔ አልላክኋቸውም' ይላል *እግዚአብሔር* 'የሐሰት ትንቢት በስሜ ይናገራሉ፤ ስለዚህ እናንተንና ትንቢት የሚናገሩላችሁን ነቢያት አሳዳለሁ፤ እናንተም ትጠፋላችሁ።' ”

[16]እኔም ለካህናቱና ለዚህ ሕዝብ ሁሉ እንዲህ አልሁ፤ “*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ '*የእግዚአብሔር* ቤት ዕቃ ከባቢሎን ቶሎ ይመለሳል' የሚሏችሁን ነቢያት አትስሟቸው፤ የሚነግሯችሁ የሐሰት ትንቢት ነውና። [17]ስለዚህ እነርሱን መስማት ትታችሁ ለባቢሎን ንጉሥ ተገዙ፤ በሕይወትም ትኖራላችሁ፤ ባለመታዘዛችሁስ ይህቺ ከተማ ለምን ትፈራርስ? [18]እውነተኞች ነቢያት ከሆኑና በእርግጥ *የእግዚአብሔር* ቃል ካላቸው፣ *በእግዚአብሔር* ቤትና በይሁዳ ንጉሥ ቤተ መንግሥት በኢየሩሳሌምም የቀሩት ዕቃዎች ወደ ባቢሎን እንዳይወሰዱ ወደ ሰራዊት ጌታ ወደ *እግዚአብሔር* እስቲ ይማልዱ! [19]የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* በዚህች ከተማ ስለ ቀሩት፡- ዐምዶች፣ ከናስ ስለ ተሠራው ትልቁ ገንዳ፣ ስለ ተንቀሳቃሽ ማስቀመጫዎችና ስለ ሌሎቹም ዕቃዎች እንዲህ ይላልና፤ [20]የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር የይሁዳን ንጉሥ የኢዮአቄምን ልጅ ኢኮንያንን[h] ከኢየሩሳሌምና ከይሁዳ መኳንንት ጋር ማርኮ ወደ ባቢሎን በወሰደ ጊዜ እነዚህ በከተማዪቱ የቀሩ ዕቃዎች ስለ ሆኑ፣ [21]*በእግዚአብሔር* ቤትና በይሁዳ ንጉሥ ቤተ መንግሥት በኢየሩሳሌምም ስለ ቀሩት ዕቃዎች፣ የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* የሚለው እንዲህ ነው፡- [22]'ወደ ባቢሎን ይወሰዳሉ፤ እኔ እርሱን እስከምጐበኝበት ቀን ድረስ በዚያ ይቀመጣሉ' ይላል *እግዚአብሔር*፤ 'በዚያ ጊዜም እመልሳቸዋለሁ፤ ወደዚህም ስፍራ አመጣቸዋለሁ።' ”

27፥14 ኤር14፥13፤ 14፥23፥16፤ማቴ7፥15
27፥15 ኤር6፥15፤ 23፥21፤29፥9፤44፥16 ፤ማቴ15፥12-14
27፥16 1ነገ7፥48-50፤2ነገ24፥13
27፥17 ኤር23፥16፤ 42፥11
27፥18 ዘኍ21፥7፤ 1ሳሙ 7፥8
27፥19 1ነገ7፥23-26፡51፤ኤር52፥17-23
27፥20 ዘዳ28፥36፤ 2ዜና36፥10፤ኤር22፥24፤ማቴ1፥11
27፥22 2ነገ20፥17፤ 25፥13፤2ዜና36፥21፤ ኤር24፥6፤ዕዝ 7፥19
28፥1 ኢሳ9፥3፤ 2ዜና36፥11
28፥2 ኤር27፥12
28፥3 2ነገ24፥13
28፥4 2ነገ25፥30፤ ኤር22፥24-27፤ሆሴ 7፥3
28፥6 ዘካ6፥10

## ሐሰተኛው ነቢይ ሐናንያ

**28** በዚያው ዓመት የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ እንደ ነገሠ በዐራተኛው ዓመት፣ አምስተኛ ወር፣ የገባዖኑ ሰው የዓዙር ልጅ ነቢዩ ሐናንያ *በእግዚአብሔር* ቤት በካህናቱና በሕዝቡ ሁሉ ፊት እንዲህ አለኝ፤ [2]“የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'የባቢሎን ንጉሥ የጫነባችሁን ቀንበር እሰብራለሁ፤ [3]የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር *ከእግዚአብሔር* ቤት ወደ ባቢሎን የወሰዳቸውን ዕቃዎች ሁሉ በሁለት ዓመት ጊዜ ውስጥ መልሼ አመጣለሁ። [4]የይሁዳንም ንጉሥ የኢዮአቄምን ልጅ ኢኮንያንን[i] ሌሎች ከይሁዳ ወደ ባቢሎን ተማርከው የተወሰዱትንም ሁሉ ወደዚህ ስፍራ እመልሳለሁ' ይላል *እግዚአብሔር*፤ የባቢሎን ንጉሥ የጫነባቸውን ቀንበር እሰብራለሁና።' ”

[5]ነቢዩ ኤርምያስም በካህናቱና *በእግዚአብሔር* ቤት ቆመው በነበሩት ሕዝብ ሁሉ ፊት፣ ለነቢዩ ለሐናንያ እንዲህ ብሎ መለሰለት፡- [6]“አሜን፤ *እግዚአብሔር* ያድርገው፤ *የእግዚአብሔርን* ቤት ዕቃ ሁሉ፣ ተማርከው የተወሰዱትንም ምርኮኞች ሁሉ ከባቢሎን በመመለስ፣ *እግዚአብሔር* የተናገርኸውን ቃል ይፈጽም። [7]ነገር ግን ለአንተም ለዚህም ሕዝብ የምናገረውን ቃል ስማ፤

[h]20 *ኢኮንያን የኢዮአኪን* ሌላው አቻ ስም ነው
[i]4 *ወይም ኢዮአኪን ይላል።*

*ቀንበር፤* የቍ2 ማብ ይመ።

*27፥13፤* ቍ8 ይመ። *በሰይፍ፣ በራብና በመቅሠፍት፤* የ14፥12 ማብ ይመ።

*27፥14፤* ቍ10 ይመ።

*27፥15፤* 14፥14፤ 23፥21 እና ማብ ይመ።

27፥16 *'ቶሎ ... ' የሚሏችሁን ነቢያት፤* ነቢዩ ሐናንያ ይል እንደ ነበረው ማለት ነው (28፥1-3 ይመ)። *የእግዚአብሔር ቤት ዕቃ፤* አንዳንዱ ዕቃ በ605 ዓ.ቅ.ክ በምርኮ ወደ ባቢሎን ተወስዶ ነበር (ዳን1:1-2 ይመ)፤ ሌላው በ597 ዓ.ቅ.ክ (2ነገ 24፥13 ይመ)፤ የቀረው ደግሞ ወደ ፊት በ586 ዓ.ቅ.ክ (ቍ21-22፤ 52፥17-23 ይመ)።

27፥18 *እውነተኞች ነቢያት ከሆኑና ... እስቲ ይማልዱ፤* እውነተኞች ነቢያት ከሆኑና ከእግዚአብሔር ጋር የሠመረ ግንኙነት ካላቸው እስቲ ለይሁዳ ምድር በአማላጅነት ይቁሙ፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር በይሁዳ ሕዝብ ላይ ወደ ፊት የሚያመጣውን ፍርድ አስቀድሞ በኤርምያስ አፍ ተናግሮአል።

27፥19 *ዐምዶች፣ ከናስ ስለ ተሠራው ትልቁ ገንዳ ... ተንቀሳቃሽ ማስቀመጫዎች፤* 52፥17 ይመ፤ በተጨማሪም 1ነገ7፥15-37 እና ማብ ይመ።

27፥22 *ወደ ባቢሎን ይወሰዳሉ፤* ይህም የሚሆነው በ586 ዓ.ቅ.ል.ክ ላይ ነው (52፥17-23 ይመ)። *እመልሳቸዋለሁ፤* ይህ ደግሞ በ538 ዓ.ቅ.ክ እና ከዚያ በኋላ ባለው አጭር ጊዜ ውስጥ ይፈጸማል (ዕዝ1፥7-11 ይመ)።

*28፥1-17፤* እዚህ ላይ እውነተኛው ነቢይ ኤርምያስ ሐሰተኛውን ነቢይ ሐናንያን ሲፋለም ይታያል።

28፥1 *ሴዴቅያስ እንደ ነገሠ በአራተኛው ዓመት፤* ዘመኑ 593 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው። *እንደ ነገሠ፤* የ26፥1፤ የ27፥1 ማብ ይመ። *ነቢዩ፤* ይህ ቃል ለእውነተኞቹም (ቍ5:10-12:15)፣ ለሐሰተኞቹም (ቍ1:5:10:12:15:17) ነቢያት የተነገረበት ጊዜ አለ። *ሐናንያ፤* የስሙ ትርጕም፣ “እግዚአብሔር ቸር ነው” ማለት ሲሆን፣ ነቢዩ በዚህ ስም መጠራቱ ተገቢ ነው ማለት ይቻላል፤ ምክንያቱም (በተሳሳተም መንገድ ቢሆን) እግዚአብሔር የይሁዳን ምርኮና ከቤተ መቅደሱ የተወሰደውን ዕቃ በቸርነቱ መልሶ ያመጣቸዋል ብሎ የሚያምን ነቢይ ነበር (ቍ3-4:11 ይመ)። *ገባዖን፤* 41፥12:16 ይመ፤ በተጨማሪም የኢሱ9፥3 ማብ ይመ።

28፥2 *እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤* ቍ11 ይመ። ምንም እንኳ ሐናንያ ሐሰተኛ ነቢይ ቢሆንም፣ እንደ ኤርምያስ ለመሆን ሲንጠራራ ይታያል (ቍ13-14:16 ይመ፤ በተጨማሪም 23፥31 ይመ)። *ቀንበር፤* የ27፥2 ማብ ይመ።

*28፥3፤* የሐናንያ ትንበያ ከኤርምያስ ቃል ጋር ይቃረናል (27፥16-22 እና ማብ ይመ)። *በሁለት ዓመት፤* ቍ11 ይመ፤ በኤርምያስ ከተነገረው ሰባ ዓመት ጋር ያነጻጽሩ (25፥11-12፤29፥10)።

28፥4 *እመልሳለሁ፤* ይህ ኤርምያስ ከተናገረው ትንቢት ጋር ይቃረናል (22፥24-27 ይመ)፤ የኤርምያስ ቃል ግን በትክክል ተፈጽሞአል (52፥34 ይመ)። *ኢኮንያንን ... ወደ ባቢሎን ተማርከው የተወሰዱትንም፤* ይህ የሆነው በ597 ዓ.ቅ.ክ ነው። *ቀንበር፤* የ27፥2 ማብ ይመ።

*28፥6፤* 1ነገ1፥36 ይመ። *አሜን፤* 11፥5 እና ማብ ይመ። *እግዚአብሔር ያድርገው፤* ለተቃዋሚው በዚህ መልክ መልስ መስጠቱ፣ የነቢዩን የኤርምያስንና የቃሉን እውነተኝነት ያሳያል (ቍ9 ይመ)።

28፥7 *ነገር ግን፤* እንደ ተባለው በሐናንያ የተነገረው ትንቢት ቢፈጸም፣ ኤርምያስ የሚደግፈው ቢሆንም፣ ቀድሞ የነበሩ ነቢያት ደግ ደጉን ብቻ እንዳልተነበዩ ያሳስበዋል (ቍ8 ይመ)።

[8]ከአንተና ከእኔ በፊት ጥንት የተነሡ ነቢያት፣ በብዙ አገሮችና በታላላቅ መንግሥታት ላይ ስለ ጦርነት፣ ስለ ጥፋትና ስለ መቅሠፍት ትንቢት ተናግረዋል። [9]ነገር ግን ስለ ሰላም ትንቢት የተናገረ ነቢይ *እግዚአብሔር* በእውነት እንደ ላከው የሚታወቀው የተናገረው ትንቢት ሲፈጸም ነው።

[10]ነቢዩም ሐናንያ ቀንበሩን ከነቢዩ ኤርምያስ ዐንገት ወስዶ ሰበረው፤ [11]በሕዝቡም ፊት፣ "*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'በሁለት ዓመት ጊዜ ውስጥ የባቢሎንን ንጉሥ የናቡከደናፆርን ቀንበር ከሕዝቡ ሁሉ ጫንቃ ላይ ልክ እንደዚህ እሰብራለሁ' አለ። በዚህ ጊዜ፣ ነቢዩ ኤርምያስ ትቶት መንገዱን ቀጠለ።

[12]ነቢዩም ሐናንያ ቀንበሩን ከነቢዩ ከኤርምያስ አንገት ወስዶ ከሰበረ ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣ የ*እግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [13]"ሄደህ ለሐናንያ እንዲህ ብለህ ንገረው፤ '*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ አንተ የዕንጨት ቀንበር ሰብረሃል፤ እኔ ግን በምትኩ የብረት ቀንበር እሠራለሁ። [14]የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ የባቢሎንን ንጉሥ ናቡከደነፆርን እንዲያገለግሉ፣ በእነዚህ ሕዝቦች ላይ የብረት ቀንበር አደርጋለሁ፤ እነርሱም ይገዙለታል፤ በዱር አራዊት ላይ እንኳ ሥልጣን እሰጠዋለሁ።' "

[15]ነቢዩ ኤርምያስም ለነቢዩ ሐናንያ እንዲህ አለው፤ "ሐናንያ ሆይ፤ ስማ! *እግዚአብሔር* ሳይልክህ ይህ ሕዝብ በሐሰት እንዲታመን አድርገሃል፤ [16]ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፦ 'ከምድር ገጽ አስወግድሃለሁ፤ *በእግዚአብሔርም* ላይ ዐመፅ ተናግረሃልና፣ በዚህ ዓመት ትሞታለህ።'"

[17]ነቢዩም ሐናንያ በዚያው ዓመት በሰባተኛው ወር ሞተ።

28፥8 ዘሌ26፥14-17፤ኢሳ5፥5-7፤ናሆ 1፥14
28፥9 ዘዳ18፥22፤ ሕዝ33፥33
28፥10 ዘሌ26፥13፤ 1ነገ22፥11
28፥11 ኤር14፥14፤ 27፥10
28፥14 ዘዳ28፥48፤ ኤር15፥12፤25፥11፤ 27፥6፤39፥11፤ዳን1፥1፤ 5፥18
28፥15 ኤር7፥4፤ 20፥6፤29፥21፡31፤ ሰቆ2፥14፤ሕዝ 13፥6
28፥16 ዘፍ7፥4፤ ዘዳ13፥5፤18፥20፤ ኤር29፥32፤ዘካ13፥3
28፥17 2ነገ1፥17
29፥1 ቍ-28፤2ዜና 36፥10፤ኤር13፥17
29፥2 2ነገ24፥8፡12
29፥4 ኤር24፥5
29፥5 ቍ-28
29፥6 ኤር30፥19

## በምርኮ ላሉት የተላከ ደብዳቤ

**29** ነቢዩ ኤርምያስ በምርኮ ተወስደው በሕይወት ለቀሩት ሽማግሌዎች፣ ለካህናቱ፣ ለነቢያቱና ናቡከደነፆር ከኢየሩሳሌም ወደ ባቢሎን ማርኮ ለወሰዳቸው ሕዝብ ሁሉ የላከው የደብዳቤ ቃል ይህ ነው፤ [2]ይህም የሆነው ንጉሡ ኢኮንያን* እቴጌዪቱ እናቱ፣ የቤተ መንግሥቱ ባለሟሎች፣ የይሁዳና የኢየሩሳሌም መሪዎች፣ እናጺዎችና ብረት ቀጥቃጮች ተማርከው ከኢየሩሳሌም ከተወሰዱ በኋላ ነበር። [3]ደብዳቤውንም ከይሁዳ ንጉሥ ከሴዴቅያስ ወደ ባቢሎን ንጉሥ ወደ ናቡከደነፆር በተላኩት መልእክተኞች በሳፋን ልጅ በኤልዓሣና በኬልቅያስ ልጅ በገማርያ እጅ ላከው፤ ደብዳቤውም እንዲህ የሚል ነበር፤

[4]የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር*፣ ከኢየሩሳሌም ወደ ባቢሎን ላስማረካቸው ሁሉ እንዲህ ይላል፤ [5]"ቤት ሠርታችሁ ተቀመጡ፤ አትክልት ተክላችሁ ፍሬውን ብሉ፤ [6]አግብታችሁ ወንዶችና ሴቶች ልጆችን ውለዱ፤ ወንዶች ልጆቻችሁንና ሴቶች ልጆቻችሁን አጋቡ፤ እነርሱም

*2 ኢኮንያን የኢዮአኪን ሌላው ስም ነው

28፥8 *ጦርነት ... ጥፋትና ... መቅሠፍት*፤ ኤርምያስ በአንድነት የሚገልጣቸው ሃሳቡ የተለመዱ ቃላት እዚህ ላይ ተገቢ የሆነ ለውጥ ተደርጎባቸው ቀርበዋል (የ14፥12 ማብ ይመ)።

28፥9 *ሰላም፤* ብዙውን ጊዜ ይህ ቃል የሐሰተኞቹ ነቢያት መልእክት ነው (6፥14 እና ማብ ይመ)።

28፥10 *ቀንበሩን ከነቢዩ ... አንገት*፤ የ27፥2 ማብ ይመ። *ሰበረው፤* ምናልባት ኤርምያስ ቀደም ሲል የተናገረውን የትንቢት ኀይለ ቃል ለመስበር እንደ ምልክት መጠቀሙ ይሆናል (25፥11-12፤ 27፥7 ይመ)፤ የኤርምያስም ቃል የእርሱን የሚቃረን ነበርና።

28፥11 *ሁለት ዓመት፤* የቍ3 ማብ ይመ።

28፥13 *የብረት ቀንበር*፤ ከእንጨት የተሠራና እጅ የመስጠት ምልክት የሆነው ቀንበር (የ27፥2 ማብ ይመ) ከብረት ወደ ተሠራውና የባርነት ምልክት ወደ ሆነው ቀንበር ይለወጣል ማለት ነው (ቍ14፤ 38፥17-23 ይመ)።

28፥14 *በእነዚህ ሕዝቦች ላይ ... ይገዙለታል፤* 27፥7 ይመ። *በዱር አራዊት ላይ እንኳ ሥልጣን*፤ 27፥6 እና ማብ ይመ።

28፥15 *እግዚአብሔር ሳይልክህ*፤ የሐሰተኞች ነቢያት ተግባር አንዱ እግዚአብሔር ሳይልካቸው ተልከናል ማለታቸው ነው (23፥21 እና ማብ ይመ)።

28፥16 *አስወግድሃለሁ፤* በቍ15 ላይ በዕብራይስጡ "ሳይልክህ" የሚለውና ይኸኛው ሥርወ ቃላቸው አንድ ነው። ትንቢት እንዲናገር እግዚአብሔር ሐናንያን "አልላከውም"፤ ስለዚህ በቅርቡ ወደ ሞት "ይላካል"። *ዐመፅ ተናግረሃልና*፤ ሐሰተኞች ነቢያት የሚፈጽሙት ይህ ዐይነቱ ድርጊት በሞት የሚያስቀጣ ነበር (ዘዳ13፥5 ይመ፤ በተጨማሪም ዘዳ18፥20 ይመ፤ ከሕዝ 11፥13፤ ከሐሥ5፥1-11 ጋር ያነጻጽሩ)።

28፥17 *ሐናንያ ... በሰባተኛው ወር ሞተ*፤ በሐሰት፣ "በሁለት ዓመት ጊዜ ውስጥ" (ቍ3:11)ሰውና ንብረት ከምርኮ ይመለሳል ብሎ የነበረው ሐናንያ ራሱ በሁለት ወር ጊዜ ውስጥ ሞተ (ቍ1 ይመ)።

*29፥1-32፤* በዚህ ክፍል ኤርምያስ በ597 ዓ.ቅ.ክ ላይ ተማርከው ለተወሰዱት የይሁዳ ሰዎች ከላከው ደብዳቤ (ቍ4-23) ቀጥሎ እግዚአብሔር በሐሰተኛው ነቢይ በሸማያ ላይ ያስተላለፈው ፍርድ (ቍ24-32) ሰፍሮ ይገኛል።

29፥2 *እቴጌይቱ እናቱ፤* ኔሁሽታ ትባላለች (2ነገ24፥8)። *እናጺዎችና ብረት ቀጥቃጮች*፤ 24፥1 እና ማብ ይመ።

29፥3 *ደብዳቤውንም በ ... እጅ ላከው፤* በዘመናችን አንድ ከበድ ያለ ጉዳይ የያዘ የመንግሥት ሰነድ በሚላክበት ሁኔታ፣ ይህም ደብዳቤ ወደላከበት ቦታ እንዲደርስ አስፈላጊው ጥንቃቄ ተደርጎአል። *ሳፋን፤* ይህ ሰው ምናልባት የአኪቃም አባት (26፥24 እና ማብ ይመ)፣ ወይም የገማርያ አባት ሳይሆን አይቀርም (36፥10 ይመ)፤ ሁለቱም ኤርምያስንና ዐላማውን የሚደግፉ ነበሩ። *ኬልቅያስ*፤ ምናልባት በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት ሊቀ ካህናት የነበረው ሰው ሊሆን ይችላል (አንድ ወይም ሁለት ሳፋን የተባሉ ሰዎች ከኬልቅያስ ጋር የተጠቀሱበትን 2ነገ 22፥12 ይመ)። *ከሴዴቅያስ ... ወደ ናቡከደነፆር በተላኩት*፤ ምናልባት ሴዴቅያስ ራሱ ለአጭር ጊዜ ወደ ባቢሎን በሄደበት ጊዜ (51፥59 ይመ)፣ አብረው የሄዱ ወይም በዚያኑ ወቅት አካባቢ (593 ዓ.ቅ.ክ ላይ) ሄደው ሊሆን ይችላል። የሄዱበት ምክንያት ግን ግልጽ አይደለም።

*29፥4፤* ተማርከው እንዲሄዱ ያደረጋቸው እግዚአብሔር እንደ መሆኑ፣ ሕዝቡ ለማረኳቸው መገዛት አላባቸው፤ ሊያምፁባቸውም አይገባም።

29፥5 *ሠርታችሁ ... ተክላችሁ*፤ የኤርምያስን መጠራት የሚያሳስቡ ቃላት ናቸው (1፥10 ይመ)፤ እዚህ ላይ ያለው ግን የቃል በቃል ትርጕም ነው። *ተቀመጡ፤* ለምሳሌ፣ ነቢዩ ሕዝቅኤል በባቢሎን ሳለ የተቀመጠው በራሱ ቤት ነበር (ሕዝ8፥1 ይመ)።

29፥6 *አግብታችሁ*፤ ጋብቻ የተፈቀደው በራሳቸው በምርኮኞቹ መካከል እንጂ የባቢሎንን ሴቶች እንዲያገቡ አልነበረም

ወንዶችና ሴቶች ልጆችን ይውለዱ፤ ቍጥራችሁም በዚያ ምድር ይብዛ እንጂ አይነስ። [7]ተማርካችሁ ለሄዳችሁባት ከተማ ሰላምና ብልጽግናን እሹ፤ ወደ *እግዚአብሔርም* ጸልዩላት፤ ምክንያቱም እርሷ ብትበለጽግ እናንተም ትበለጽጋላችሁ።" [8]የእስራኤል ስምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* በእርግጥ እንዲህ ይላልና፤ "በመካከላችሁ ያሉት ነቢያትና ጠንቋዮች አያታልሏችሁ፤ የሚያልሙላችሁንም ሕልም አትስሙ፤ [9]በስሜ ሐሰተኛ ትንቢት ይነግሯችኋል እንጂ እኔ አልላክኋቸውም" ይላል *እግዚአብሔር*።

[10]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ሰባው ዓመት የባቢሎን ቈይታችሁ በተፈጸመ ጊዜ እጐበኛችኋለሁ፤ ወደዚህም ሥፍራ ልመልሳችሁ የገባሁላችሁን መልካሚቱን ቃሌን እፈጽምላችኋለሁ። [11]ለእናንተ ያለኝን ዕቅድ እኔ ዐውቃለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "ዕቅዱም ፍጻሜው ያማረና ተስፋ የሚሰጥ፣ እናንተንም የሚጠቅም እንጂ የሚጐዳ አይደለም። [12]እናንተም ትጠሩኛላችሁ፤ ቀርባችሁ ወደ እኔ ትጸልያላችሁ፤ እኔም እሰማችኋለሁ። [13]እናንተ ትፈልጉኛላችሁ፣ በፍጹም ልባችሁም ከፈለጋችሁኝ ታገኙኛላችሁ፤ [14]እኔም እገኝላችኋለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "ከምርኮም[o] እመልሳችኋለሁ፤ እናንተንም ከበተንሁበት አገርና ስፍራ ሁሉ እመልሳችኋለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "በምርኮ ምክንያት ወዳስለቀቅኋችሁም ምድር እመልሳችኋለሁ።"

[15]እናንተም፣ "*እግዚአብሔር* በባቢሎን ነቢያት አስነሥቶልናል" ትላላችሁ፤ [16]*እግዚአብሔር* ግን በዳዊት ዙፋን ላይ ስለሚቀመጠው ንጉሥና ከእናንተ ጋር ተማርከ ስላልሄደው ወገንህ በዚህ ከተማ ስለቀረው ሕዝብ ሁሉ እንዲህ ይላል፤ [17]የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* በእርግጥ እንዲህ ይላል፤ "ሰይፍን፣ ራብንና መቅሠፍትን እሰድባቸዋለሁ፤ ከመበላሸቱ የተነሣም ሊበላ እንደማይቻል እንደ መጥፎ የበለስ ፍሬ አደርጋቸዋለሁ። [18]በሰይፍ፣ በራብና በመቅሠፍት አሳድዳቸዋለሁ፤ በምድር መንግሥታት ሁሉ ፊት የሚያስጸይፉ አደርጋቸዋለሁ፤ በማሳድዳቸውም ሕዝቦች ዘንድ የርግማንና የድንጋጤ፣የመሣቂያና የመዘባበቻ ምልክት ይሆናሉ፤ [19]በአገልጋዮቼ በነቢያት በኩል ደጋግሜ የላክሁላቸውን ቃሌን አልሰሙምና" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "እናንተ ምርኮኞችም አልሰማችሁም" ይላል *እግዚአብሔር*።

[20]"ስለዚህ ከኢየሩሳሌም ወደ ባቢሎን የሰደድኋችሁ ምርኮኞች ሁሉ፣ የ*እግዚአብሔርን* ቃል ስሙ። [21]የእስራኤል ስምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* በስሜ የሐሰት ትንቢት ስለሚነግሯችሁ ስለ ቆላያ ልጅ ስለ አክዓብና ስለ መዕሤያ ልጅ ስለ ሴዴቅያስ እንዲህ ይላል፤ 'እነዚህን ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደናፆር አሳልፌ እሰጣቸዋለሁ፤ እርሱም ዐይናችሁ እያየ ይገድላቸዋል። [22]በእነርሱ ላይ ከደረሰው የተነሣ በባቢሎን ያሉ የይሁዳ ምርኮኞች ሁሉ፣ "*እግዚአብሔር* የባቢሎን ንጉሥ በእሳት እንደ ጠበሳቸው እንደ ሴዴቅያስና እንደ አክዓብ ያድርግብህ" ብለው ይራገማሉ፤ [23]ከባልንጀሮቻቸው ሚስቶች ጋር በማመንዘርና ያልነገርኋቸውን ቃል በስሜ በሐሰት በመናገር በእስራኤል ዘንድ በደል ፈጽመዋ

[o]14 *ወይም ዕድል ፈንታችሁን እመልስላችኋለሁ*

29፥7 ዕዝ6፥10፤ 1ጢሞ2፥1-2
29፥8 ዘዳ13፥1፤ ኤር23፥25:27፤ 37፥9፤1ዮሐ4፥1
29፥9 ኤር23፥21፤ 27፥15፤ሰቆ2፥14፤ሕዝ 13፥6
29፥10 ሩት1፥6፤ 1ነገ8፥56፤2ዜና36፥ 21፤ኤር16፥14፤24፥6 ፤32፥42፤33፥14፤ዳን 9፥2
29፥11 ኢዮ8፥7፤ መዝ40፥5፤ኢሳ55፥12 ፤ዘካ8፥15
29፥12 1ነገ8፥30፤ መዝ145፥19፤ኢሳ 55፥6፤ሆሴ2፥23፤ሶፎ 3፥12፤ዘካ13፥9
29፥13 ዘዳ4፥29፤ 2ዜና6፥37፤ማቴ7፥7
29፥14 ዘዳ30፥3፤ ኤር23፥3-4፤30፥3:10 ፤46፥27፤ሕዝ37፥21፤ 39፥25፤አሞ9፥14፤ ሶፎ3፥20
29፥17 ኢሳ5፥4፤ ኤር27፥8
29፥18 ዘኍ5፥27፤ ዘዳ28፥25:37፤ኢሳ 28፥22፤ኤር15፥4፤ 18፥16፤22፥10፤ 44፥12፤ሚክ 2፥6
29፥19 ኤር6፥19፤ 7፥25፤25፥4
29፥20 ኤር24፥5
29፥21 ቍ9፤ኤር 14፥14
29፥22 ዳን3፥6
29፥23 ዘፍ31፥48፤ ኤር7፥11፤23፥14፤ዕብ 4፥13

(ከዘዳ7፥3-4፤ ከዕዝ9፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ)።

*29፥7፤* በዚህ ቍጥር ላይ ያለው ሐሳብ በጥንታዊው ዓለም አመለካከት ያንጸባርቃል ማርኮ የወሰደውን በቅንነት ማገልገልና እርሱም ብልጽግና መለመን አልተለመደም። *ሰላምና ብልጽግና ... ብትበለጽግ ... ትበለጽጋላችሁ፤* ዕብራይስጡ ሦስቱንም ቃላት "ሻሎም፣ ሻሎም፣ ሻሎም" ብሎአቸዋል። *ከተማ፤* ምርኮኞቹ የተቀመጡባቸውን ቦታዎች ሁሉ የሚያመለክት ነው። *ጸልዩላት፤* ዕዝ6፥10 እና ማብ፤ ማቴ5፥44 ይመ።

29፥8 *ነቢያትና ... ሕልም፤* 27፥9 እና ማብ ይመ። *በመካከላችሁ፤* ባቢሎን በነበሩት ምርኮኞችም መካከል ሐሰተኞች ነቢያት ነበሩ ማለት ነው (ቍ21:31 ይመ)፤ እነዚህም ሕዝቡ በ597 ዓ.ቅ.ክ ላይ ተማርኮ ሲሄድ አብረው የሄዱ መሆናቸው አያጠራጥርም።

*29፥9፤* ቍ31 ይመ። በተጨማሪም የ23፥16:21 ማብ ይመ።

29፥10 *ሰባው ዓመት፤* የ25፥11-12 ማብ ይመ። *ልመልሳችሁ፤* የ27፥22 ማብ ይመ።

29፥11 *ዐውቃለሁ፤* ቍ23 ይመ። ሁኔታዎቹ ያማሩና የሠመሩ መስለው ባይታዩም፣ እግዚአብሔር ሕዝቡን አልረሳም። *የሚጠቅም፤* የቍ7 ማብ ይመ። *የሚጐዳ አይደለም፤* እግዚአብሔር ብልጽግናንም፣ ጥፋትንም ለማምጣት ሁሉ በእጁ ነው (ኢሳ 45፥7 ይመ)።

*29፥12-13፤* በዘዳ4፥29-30 የሚገኘው ሐሳብ በዚህ ክፍል ተንጸባርቆአል። እግዚአብሔር ለሕዝቡ ለመስጠት የሚፈልገው መልካም ነገር እውን ሊሆን የሚችለው ሕዝቡ በንስሐ ለመመለስ ፈቃደኛ ሲሆን ብቻ ነው።

*29፥14፤* የዘዳ 30፥3-5 ሐሳብ እዚህ ላይ በአጭሩ ቀርቦአል። *ከምርኮም እመልሳችኋለሁ፤* አንዳንዶቹ "ምርኮአችሁን እመልሳለሁ" ማለቱ ነው ሲሉ ይተረጕሙታል። በተጨማሪ 30፥3:18፤ 31፥23፤ 32፥44፤ 33፥7:11:26፤ 48፥47፤ 49፥6:39፤ የመዝ126፥4 ማብ ይመ። በዕብራይስጥ፣ "መመለስ" የሚለው ቃል "ምርኮ" ከሚለው ጋር እጅግ ተመሳሳይ ነው።

29፥15 *በባቢሎን ነቢያት፤* የቍ8 ማብ ይመ።

29፥16 *በዳዊት ዙፋን ላይ ... ንጉሥና፤* ሴዴቅያስን ማለት ነው። *ስለሚቀመጠው ... ስላልሄደው፤* በዕብራይስጡ ለሁለቱም የገባው ቃል አንድ ዐይነት ነው። ንጉሡም ሕዝቡም እኩል በደለኞች ነበሩ።

29፥17 *ሰይፍን፣ ራብንና፣ መቅሠፍትን፤* ቍ18 ይመ፤ በተጨማሪም የ14፥12 ማብ ይመ። *ከመበላሸቱ የተነሣ ሊበላ እንደማይችል እንደ መጥፎ የበለስ ፍሬ፤* 24፥8 ይመ።

*29፥18፤* 24፥9 እና ማብ ይመ።

29፥19 *ደጋግሜ፤* የ7፥13 ማብ ይመ። *በአገልጋዮቼ በነቢያት፤* የ7፥25 ማብ ይመ። *እናንተ ምርኮኞችም አልሰማችሁም፤* ሕዝ2፥5:7፤ 3፥7:11 ይመ።

29፥21 *አክዓብና ... ሴዴቅያስ፤* የታወቁት ሁለት የእስራኤልና የይሁዳ ነገሥታት ሳይሆኑ፣ ይልቁንም ሐሰተኞች ነቢያት ናቸው (የቍ8 ማብ ይመ)።

29፥22 *ጠበሳቸው ... ይራገማሉ፤* በዕብራይስጡ የሁለቱ ቃላት ድምፀት ከአክዓብ አባት "ከቆላያ" ጋር ይመሳሰላል (በአማርኛ "መቁላት" ከሚለው ቃል ጋር ይመሳሰላል)። *በእሳት፤* በባቢሎን ምድር ወንጀለኛ በዚህ ዘዴ ይቀጣ ነበር (ዳን3፥6:24 ይመ)።

29፥23 *በእስራኤል ዘንድ በደል ፈጽመዋልና፤* ዘፍ34፥7 እና ማብ ይመ። *በማመንዘርና ... በሐሰት በመናገር፤* የ23፥10 ማብ ይመ። *ዐውቃለሁ፤* ቍ11 ይመ።

ልና:: ይህንም እኔ ዐውቃለሁ፤ ምስክር ነኝ' " ይላል እግዚአብሔር::

### ለሸማያ የተላከ መልእክት

[24]"ለኔሔላማዊው ለሸማያ እንዲህ ብለህ ንገረው፤ [25]'የእስራኤል ስምባከ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ በኢየሩ ሳሌም ላለው ሕዝብ ሁሉ፣ ለካህኑ ለመዕ ሤያ ልጅ ለሶፎንያስና ለሌሎችም ካህናት ሁሉ በገዛ ስምህ ደብዳቤዎችን ልከሃል፤ ለሶፎንያስም እንዲህ ብለሃል፤ [26]"በእግዚ አብሔር ቤት ኀላፊ ትሆን ዘንድ እግዚ አብሔር በካህኑ በዮዳሄ ምትክ ካህን አድ ርጎ ሾሞሃል፤ ነቢይ ነኝ እያለ ትንቢት የሚናገር ማንኛውም ያበደ ሰው እግሩን በግንድ፣ ዐንገቱን በሰንሰለት መቀፍደድ ይገባሃል:: [27]ታዲያ፣ ነቢይ ነኝ ባዩን የዓ ናቶቱን ኤርምያስን ለምን አልገሠጽኸውም? [28]ይህ ሰው፣ 'የምርኮው ጊዜ ረዥም ስለ ሆነ፣ ቤት ሠርታችሁ ተቀመጡ፤ አት ክልትም ተክላችሁ ፍሬውን ብሉ' በማለት ወደ ባቢሎን መልእክት ልኮብናል::" ' "

[29]ካህኑ ሶፎንያስም ደብዳቤውን ለነቢዩ ኤርምያስ አነበበለት:: [30]የእግዚአብሔርም ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [31]"ይህን መልእክት በምርኮ ላሉት ሁሉ እንዲህ ብለህ ላክ፤ 'ስለ ኔሔላማዊው ስለ ሸማያ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "እኔ ሳልልከው ሸማያ ትንቢት ተናግሮላችሁ፣ በሐሰት እንድትታመኑ አድርጎአችኋልና፣

29፥25 2ነገ25፥18
29፥26 1ሳሙ10፥11፤ኤር20፥2፤ሆሴ 9፥7፤ዮሐ10፥20
29፥28 ቍ1፥5፥10
29፥29 ኤር21፥1
29፥31 ቍ24፤ ኤር14፥14
29፥32 ቍ10፤ 1ሳሙ2፥30-33፤ኤር 28፥16
30፥2 ኢሳ30፥8፤ ኤር36፥2
30፥3 ኤር16፥14፡ 15፤24፥6፤29፥14
30፥5 ኤር6፥25
30፥6 ኢሳ29፥22፤ ኤር4፥31
30፥7 ቍ10፤ኢሳ 2፥12፤22፥5፤ኤር 23፥3፤ሶፍ1፥15

[32]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "እነሆ፣ ኔሔላማዊውን ሸማያንና ዘሩን እቀጣለሁ፤ በእኔ ላይ ዐመፅን ተናግሮአልና፣ በዚህ ሕዝብ መካከል የሚተርፍ ዘር አይኖረውም" ' ይላል እግዚአብሔር፤ 'ለሕዝቤ የማደርገው ንም መልካም ነገር አያይም::' "

### የእስራኤል ሕዝብ መመለስ

**30** ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ ኤርም ያስ የመጣው ቃል ይህ ነው፤ [2]"የእ ስራኤል ስምባከ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'የነገርሁህን ቃል ሁሉ በመጽሐፍ ጻፈው:: [3]እነሆ፣ ሕዝቤን እስራኤልንና ይሁዳን' ይላል እግዚአብሔር፤ 'ለአባቶቻቸው ወደ ሰጠኋት ምድር የምመልስበት ጊዜ ተቃር ቦአል፤' እነርሱም ይወርሷታል' ይላል እግዚ አብሔር::'

[4]እግዚአብሔር ስለ እስራኤልና ስለ ይሁዳ የተናገረው ቃል ይህ ነው፤ [5]"እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

" 'የፍርሀትና የሽብር ጩኸት ተሰምቶአል፤
ሰላምም የለም::
[6]እስቲ ጠይቁ፤ ተመልከቱም፤
ወንድ መውለድ ይችላል?
ታዲያ ወንድ ሁሉ ምጥ እንደ ያዛት ሴት፣
እጁን በሆዱ ላይ አድርጎ፣
የሰውስ ሁሉ ፊት ጠቍሮ የማየው
ለምንድን ነው?
[7]ያ ቀን ምንኛ አስጨናቂ ይሆናል!
እንደዚያም ያለ አይኖርም፤

29፥24 *ሸማያ፤* ሐሰተኛ ነቢይ ነው (ቍ31 ይመ):: *ኔሔላ ማዊው፤* በዕብራይስጡ ይህ ቃል በቍ8 ላይ "ሕልም" ተብሎ ከተተረጐመው ቃል ጋር አንድ ነው (27፥9 እና ማብ ይመ፤ በአ ማርኛም ተመሳሳይ እንደ ሆነ ያስተውሉ)::

29፥25 *ሶፎንያስ፤* ነቢዩ ሶፎንያስ አይደለም፤ (የ21፥1 ማብ ይመ)::

29፥26 *ዮዳሄ፤* በንጉሡ በኢዮአስ ዘመን ከነበረው ካህን ጋር አንድ አይደለም፤ ስመ ሞክሼ ነው (2ነገ12፥7 ይመ):: *በእግዚአብሔር ቤት ኀላፊ፤* የ20፥1 ማብ ይመ:: *ያበደ ሰው፤* የቢያትን ባሕርይ ድንገት ለሚመለከት ሰው አንዳንድ ጊዜ ንክ መስለው ሊታዩ ይችላሉ (2ነገ9፥11 ይመ):: *ግንድ፤* የ20፥2 ማብ ይመ::

29፥27 *የዓናቶቱ፤* የ1፥1 ማብ ይመ::

*29፥28፤* ቍ5 እና ማብ ይመ:: *የምርኮው ጊዜ ረዥም፤* እዚህ ላይ ሰባ ዓመት ማለት ነው (25፥11-12 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 2ሳሙ3፥1 ይመ)::

29፥29 *ሶፎንያስም፤* ለኤርምያስ በጎ አመለካከት ያለው ይመስላል (21፥1-2፤ 37፥3 ይመ)::

*29፥31-32፤* እግዚአብሔር በሸማያ ላይ ያደረገው በሐናንያ ላይ ካደረገው ጋር ይመሳሰላል (28፥15-16 ይመ)::

29፥31 *በሐሰት እንድትታመኑ አድርጎአችኋል፤* 28፥15 ይመ::

29፥32 *ዐመፅን ተናግሮአልና፤* 28፥16 እና ማብ ይመ::

*30፥1-33፥26፤* ይህ ክፍል በትንቢተ ኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ፣ "የመጽናናት መጽሐፍ" ተብሎ ይታወቃል፤ ይኸውም የእስራኤልን (የሰሜኑን) እና የይሁዳን (የደቡቡን) መንግሥት ተመልሶ እንደ ሕዝብ የማቋቋም ትንቢተ ስላዘለ ነው:: ትንቢቱ በሁለት መልክ የሚታይ ነው፤ የመጀመሪያው በቅርቡ ስለሚ ሆነው የአይሁድ ሕዝብ ከባቢሎን ምርኮ መመለስ የሚገልጽ ሲሆን፣ ሁለተኛው ስለ መሲሑ መምጣት የሚናገር ነው:: የእግዚአብሔ ርን ሕዝብ የወደፊት ተስፋ በተመለከተ በኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ ወጥ ሐሳብ ይዞ በረዥሙ በመቅረቡ፣ ይህ ክፍል ወደር አይገኝለትም (ስለ 'መመለስ' በአጭሩ የተጠቀሰባቸውን ሌሎች ክፍሎች 3፥14-18፤ 16፥14-15፤ 23፥3-8፤ 24፥4-7 ይመ):: በ32፥1 ላይ የሚገኘው ሐሳብ፣ ይህ ክፍል የተጻፈው በ 587 ዓ. ቅ.ክ ላይ ለመሆኑ ፍንጭ ይሰጣል፤ ይኸውም ናቡከደነፆር ኢየሩ ሳሌምን ከማጥፋቱና ሕዝቧም በምርኮ ወደ ባቢሎን ከመፍለሱ አንድ ዓመት በፊት ነው::

*30፥1-31፥40፤* በዚህ ክፍል የሚገኙት ሁለት ምዕራፎች በሞላ የተጻፉት በግጥም ነው፤ ነቢዩ፣ እግዚአብሔር ሕዝቡን የሚታደግበትን ወቅት ከሩቅ እየተመለከተ የጻፈው እንደ መሆ ኑ፣ ምዕራፎቹ በብሩህ ተስፋ የተሞሉ ናቸው::

*30፥1፤* በዚህ ቍጥር ላይ ያለው ዐረፍተ ነገር ለም30-31 ርእስ ይሆናል (ምናልባትም ለም32-33 ጭምር ርእስ ሊሆን ይችላል)::

30፥2 *ጻፈው፤* ከምርኮ የመመለሱን ትንቢት ለመጪ ትውልድ ለማቆየት ማለት ነው:: *በመጽሐፍ፤* በጥቅልል ብራና መልክ የተዘጋጀ ማለት ነው (ለምሳሌ:- 36፥2፡4፤ 45፥1 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፀ17፥14 ማብ ይመ):: *የነገርሁህን ቃል ሁሉ፤* ወደ ፊት የእግዚአብሔር ሕዝብ የሚያገኙትን የመቤዠት ተስፋ ማለት ነው:: እዚህ ቍጥር ላይ ያለው ሐሳብ በ36፥2 በዝርዝር እንደ ቀረበው በግልጽ የተብራራ አይደለም::

30፥3 *የምመልስበት፤* አንዳንዶች፣ "ምርኮአችሁን እመልሳ ለሁ" በማለት ይህን ሐረግ ይተረጕሙታል (የ29፥14 ማብ ይመ):: *እስራኤልንና ይሁዳን፤* የሰሜኑንና የደቡቡን መንግሥታት ማለት ነው፤ ከእነዚህም የመጀመሪያው በ721 ዓ.ቅ.ክ ላይ በምርኮ ተወስዶአል፤ ሁለተኛው ደግሞ ተማርኮ ለመሄድ፣ የቀረው የአንድ ዓመት ጊዜ ብቻ ነው (የ30፥1-33፥26 ማብ ይመ)::

30፥5 *የፍርሀትና የሽብር ጩኸት፤* የጦርነትና የጥፋት ውካታ ድምፅ ማለት ነው::

30፥6 *ምጥ እንደ ያዛት፤* የመጨነቅ የመጠበብ ምልክት ነው (የ4፥19 ማብ ይመ)::

*30፥7፤* የጌታን ቀን የሚያመለክት ገለጻ ነው (የኢሳ 2፥11፡17፡20፤ የአሞ5፥18፤ 8፥9 ማብ ይመ):: ኤርምያስ እዚህ ላይ የሚናገረው በቅርቡ ስለሚፈጸም ጕዳይ ነው (ቍ8:18 ይመ)፤ ሆኖም በመሲሑ ዘመን የሚሆነውን የሩቅ ጊዜ ሁናቴም ያመ ለክታል:: *አስጨናቂ፤* በዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም፣

ለያዕቆብ የመከራ ጊዜ ነው፤
ነገር ግን ይተርፋል።

[8]“ ‘በዚያን ቀን’ ይላል የሰራዊት ጌታ
*እግዚአብሔር*፤
‘በጫንቃቸው ላይ ያለውን ቀንበር
እሰብራለሁ፤
እስራታቸውንም እበጥሳለሁ፤
ከእንግዲህ ባዕዳን አይገዙአቸውም።
[9]ነገር ግን በስምባቸው *ለእግዚአብሔር*፣
ለማስነሣላቸውም ለንጉሣቸው፣
ለዳዊት ይገዛሉ።
[10]“ ‘ስለዚህ፤ አገልጋዬ ያዕቆብ ሆይ፤
አትፍራ፤
እስራኤል ሆይ፤ አትደንግጥ፤’
ይላል *እግዚአብሔር*፤
‘አንተን ከሩቅ አገር፣
ዘርህንም ከተማረኩበት ምድር
እታደጋለሁ፤
ያዕቆብ ተመልሶ በሰላምና በእርጋታ
ይቀመጣል፣
የሚያስፈራውም አይኖርም።
[11]እኔ ከአንተ ጋር ነኝ፤ አድንሃለሁም፣
ይላል *እግዚአብሔር*፤
‘በአሕዛብ መካከል በትኜሃለሁ፤
እነዚህን አሕዛብ ሁሉ ፈጽሜ
አጠፋለሁ፤
አንተን ግን ሙሉ በሙሉ አላጠፋህም፤
በመጠኑ እቀጣሃለሁ እንጂ፣
ያለ ቅጣት አልተውህም።
[12]“*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
“ ‘ስብራትህ የማይጠገን፣
ቍስልህም የማይድን ነው።
[13]የሚሟገትልህ ሰው የለም፤
ለቍስልህ መድኃኒት አይኖርም፤
ፈውስም አታገኝም።
[14]ወዳጆችህ ሁሉ ረስተውሃል፤
ስለ አንተም ግድ የላቸውም።
ጠላት እንደሚመታ መታሁህ፤
እንደ ጨካኝም ቀጣሁህ፤
በደልህ ታላቅ፣
ኀጢአትህም ብዙ ነውና።
[15]ፈውስ ለማይገኝለት ሕመምህ፣
ስለቍስልህ ለምን ትጮኻለህ?
በደልህ ታላቅ፣ ኀጢአትህም ብዙ ስለሆነ፣
እነዚህን ሁሉ አድርጌብሃለሁና።
[16]“ ‘ነገር ግን አሟጠው የበሉህ ሁሉ
እንደዚያው ይበላሉ፤
ጠላቶችህ ሁሉ ለምርኮ ዐልፈው
ይሰጣሉ፤
የሚዘርፉህ ይዘረፋሉ፤
የሚበዘብዙህም ሁሉ ይበዘበዛሉ።
[17]አንተን ግን መልሼ ጤነኛ አደርግሃለሁ፤
ቍስልህንም እፈውሳለሁ፤’
ይላል *እግዚአብሔር*።
“ ‘የተናቀች፣
ማንም የማይፈልጋት ጽዮን”
ብለውሃልና።’
[18]“*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
“ ‘እነሆ የያዕቆብን ድንኳን ምርኮ
እመልሳለሁ፤
ለማደሪያውም እራራለሁ፤
ከተማዪቱ በፍርስራሿ ጒብታ ላይ
ትሠራለች፤
ቤተ መንግሥቱም በቀድሞ ቦታው
ይቆማል።

30፥8 መዝ107፥14፤ኢሳ9፥4፤ኤር25፥14፤27፥7፤ሕዝ34፥27
30፥9 ቍ21፤1ሳሙ13፥14፤ኤር33፥15፤ሕዝ34፥23-24፤37፥24፤ሆሴ1፥11፤3፥5፤ማቴ1፥1
30፥10 ቍ7፤ኢሳ35፥9፤41፥10፤44፥2፤ኤር17፥25፤23፥4፤29፥14፡22፤54፥4፤ሕዝ34፥25-28
30፥11 ዘሌ26፥44፤ኢሱ1፥5፤ኤር5፥18፤10፥24፤46፥28፤ሆሴ11፥9፤አሞ9፥8
30፥12 ኢዮ6፥4፤ኤር8፥22፤10፥19
30፥13 መሳ6፥31፤ኤር8፥22፤14፥19፤46፥11፤ናሆ3፥19
30፥14 ኢዮ13፥24፤30፥21፤ኤር22፥20፤25፥7፤ሰቆ1፥2
30፥15 ምሳ1፥31፤ኤር10፥19፤ሰቆ 1፥5
30፥16 ኢሳ14፥2፤29፥8፤33፥1፤ኤር2፥3፤49፥2፤50፥10፤ኢል3፥4-8
30፥17 መዝ142፥4፤ኢሳ1፥5፤6፥12፤ኤር33፥24፤ሆሴ6፥1
30፥18 ቍ3፤ዘኍ24፥5፤ዘዳ30፥3፤መዝ102፥13፤ኤር31፥4፡23፡24፡38፤32፥44፤33፥7፡26፤ሕዝ36፥10፡33፤39፥25፤አሞ9፥14

[a]3 ወይም *የሕዝቤን የእስራኤልንና የይሁዳን ዕድል ፈንታ እመልሳለሁ*

“ታላቅ” ማለት ይሆናል (ኢል2፥11፤ ሶፎ1፥14 እንደተገለጠው ማለት ነው፤ ከኢል1፥15 ጋር ያነጻጽሩ)። *እንደዚያም ያለ አይኖርም*፤ ዳን12፥1፤ኢል2፥2፤ማቴ24፥21 ይመ። *የመከራ ጊዜ*፤ ዕብራይስጡ ይህን ሐረግ በዳን12፥1 ላይ “የመከራ ዘመን” ይለዋል (ማቴ24፥21 እና ማብ፤ ራእ16፥18 ይመ)። *ለያዕቆብ*፤ ለእስራኤል ሕዝብ ማለት ነው (ቍ10 ይመ)።

30፥8 *በዚያ ቀን*፤ የኢሳ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ። *ቀንበር*፤ የ27፥2 ማብ ይመ። *እስራታቸውንም እበጥሳለሁ*፤ የባርነትን ሰንሰለት ፈትቶ እግዚአብሔር ሕዝቡን ከአሕዛብ ባርነት ነፃ እንደሚያወጣ ተስፋ ይሰጣቸዋል (ከመዝ2፥3 ጋር ያነጻጽሩ)። *ባዕዳን*፤ ባቢሎናውያንን ብቻ ሳይሆን ሌሎችንም ሕዝቦች ያመለክታል።

30፥9 *ለንጉሣቸው ለዳዊት*፤ መሲሑን ክርስቶስን ለማለት እንጂ ንጉሥ ዳዊትማ የኖረበት ዘመን ከዚህ ቀደም ይላል (የ23፥5 ማብ ይመ)። ‘ታርጕም’ የተባለው ጥንታዊ የአራማይክ የብሉይ ኪዳን ትርጕም ይህን፣ “ለንጉሣቸው ለዳዊት ልጅ ለመሲሑ” ይለዋል። *ለማስነሣላቸውም*፤ የ23፥5 ማብ ይመ።

*30፥10-11*፤ በ46፥27-28 ላይ ከሞላ ጐደል እንዳለ ተደግሞ እናገኘዋለን።

30፥10 *አገልጋዬ ያዕቆብ*፤ ኢሳ41፥8-9 እና ማብ፤ 44፥1-2፡21፤ 45፥4፤ 48፥20 ይመ። *የሚያስፈራውም አይኖርም*፤ ከቍ5 ጋር ያገናዝቡ፤ ዘሌ26፥6፤ ኢዮ11፥19፤ ኢሳ17፥2፤ ሕዝ34፥28፤ 39፥26፤ ሚክ4፥4 እና ማብ፤ ሶፎ3፥13 ይመ።

30፥11 *እኔ ከአንተ ጋር ነኝ፤ አድንሃለሁም*፤ ይህ ዐረፍተ ነገር በመጀመሪያ ለራሱ ለኤርምያስ ብቻ የተነገረ ሲሆን (1፥8፡19፤ 15፥20 ይመ)፣ እዚህ ላይ የተነገረው ግን ለእግዚአብሔር ሕዝብ በሙሉ ነው። *በትኜሃለሁ*፤ 9፥16 እና ማብ፤ 23፥1-2 ይመ። *ሙሉ በሙሉ አላጠፋህም*፤ 4፥27 እና ማብ ይመ። *ያለ ቅጣት አልተውህም*፤ 25፥29፤ 49፥12 ይመ።

*30፥12-13*፤ 8፥22፤ ሆሴ5፥13፤ 6፥1፤ 7፥1፤ 11፥3 ይመ።

30፥12 *ስብራትህ ... ቍስልህም*፤ የይሁዳን ማለት ነው። *ቍስልህም የማይድን ነው*፤ 15፥18 እና ማብ ይመ። *ስብራትህ የማይጠገን*፤ 14፥17 ይመ።

30፥13 *የሚሟገትልህ*፤ ጠላቶቹን ማለት ነው። *ለቍስልህ መድኃኒት አይኖርም*፤ ሆሴ5፥13 ይመ።

30፥14 *ወዳጆችህ*፤ የ22፥20 ማብ ይመ። ለምሳሌ ባቢሎናውያን ይሁዳን እንዳያጠቋት ግብፅ ትረዳት ነበር (37፥5-7 ይመ)። *በደልህ ... ብዙ ነውና*፤ 5፥6፤ 13፥22 ይመ። ይህ ሐረግ በዕብራይስጡ በቍ15 ላይ እንዳለ ተደግሞ እናገኘዋለን።

30፥16 *አሟጠው የበሉህ ሁሉ*፤ 3፥24፤ 5፥17፤ 8፥16፤ 10፥25 ይመ። *ይበላሉ*፤ የ25፥26 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 51፥48-49 ይመ። *ይዘረፋሉ*፤ ኢሳ17፥14 ይመ።

30፥17 *መልሼ ጤነኛ አደርግሃለሁ*፤ ከ8፥22 ጋር ያገናዝቡ፤ 33፥6፤ ኢሳ58፥8 ይመ።

30፥18 *ምርኮ እመልሳለሁ*፤ የ29፥14 ማብ ይመ። *ከተማይቱ ... ቤተ መንግሥቱም*፤ ይህን ዕብራይስጡ ባልተወሰነ ነጠላ ቍጥር “ከተማ ቤተ መንግሥት” ይለዋል፤ ይህም ምናልባት ትንቢቱ በአጠቃላይ ለይሁዳ ከተሞችና አብያተ መንግሥት መነገሩን የሚያሳይ ሳይሆን አይቀርም (አሞ9፥14 ይመ)። ይሁን እንጂ እዚህ ላይ የተነገረው ስለ ኢየሩሳሌምና ስለ ቤተ መንግሥቷ ብቻ ነው ማለት ይቻላል (3፥38 ይመ)። *በፍርስራሿ*፤ ይህን ቃል ዕብራይስጡ “ቴል” ይለዋል። የሚያመለክተውም አንዱ ከተማ ጠፍቶ በፍርስራሹ ላይ ሌላ ከተማ ሲሠራበት፣ ያም በተራው እንደዚሁ ጠፍቶ በላዩ ላይ ሌላ ከተማ ሲሠራበት፣ እንዲህ እንዲህ እያለም በመጨረሻ ተቈልሎ የሚገኘውን የዚያን ሁሉ ከተማ ፍርስራሽ ክምር ነው (ለምሳሌ ኢሱ11፥13 ይመ)።

19ከእነርሱም የምስጋና መዝሙር፣
 የእልልታ ድምፅ ይሰማል።
እኔ አበዛቸዋለሁ፤
 ቍጥራቸውም አይቀንስም፣
አከብራቸዋለሁ፤
 የተናቁም አይሆኑም።
20ልጆቻቸው እንደ ቀድሞው ይሆናሉ፤
 ማኅበረ ሰቡም በፊቴ የጸና ይሆናል፤
 የሚጨቍኗቸውን ሁሉ እቀጣለሁ።
21መሪያቸው ከራሳቸው ወገን ይሆናል፤
 ገዢቸውም ከመካከላቸው ይነሣል፤
ወደ እኔ አቀርበዋለሁ፤ እርሱም
  ይቀርበኛል፤
 አለዚያማ ደፍሮ፣
ወደ እኔ የሚቀርብ ማን ነው?
  ይላል እግዚአብሔር።
22“ ‘ስለዚህ እናንተ ሕዝብ ትሆኑኛላችሁ፤
 እኔም አምላክ እሆናችኋለሁ።’ ”

23እነሆ፣ የእግዚአብሔር ማዕበል፣
 በቍጣ ይነሣል፤
የሚገለባብጥም ዐውሎ ነፋስ፣
 በክፉዎች ዐናት ላይ ይወርዳል።
24የልቡን ሐሳብ ሳይፈጽም፣
 የእግዚአብሔር ቍጣ፣
እንዲሁ አይመለስም፤
 በሚመጡትም ዘመናት፣
 ይህን ታስተውላላችሁ።

31 “በዚያ ዘመን” ይላል እግዚአብሔር፣ “ለእስራኤል ነገድ ሁሉ አምላካቸው እሆናለሁ፤ እነርሱም ሕዝቤ ይሆናሉ።”

2እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
 “ከሰይፍ የተረፈው ሕዝብ፣
በምድረ በዳ ሞገስን ያገኛል፤
 እኔም ለእስራኤል ዕረፍት ለመስጠት
  እመጣለሁ።”

3እግዚአብሔር ከሩቅ[*] ተገለጠልን፤ እንዲህም አለን፤

“በዘላለማዊ ፍቅር ወድጄሻለሁ፤
 ስለዚህም በርኅራኄ ሳብሁሽ።
4የእስራኤል ድንግል ሆይ፤ እንደ ገና
  አንጽሻለሁ፤
 አንቺም ትታነጪያለሽ፤
ከበሮችሽንም እንደ ገና አንሥተሽ፣
 ከሚፈነጥዙት ጋር ትፈነድቂያለሽ።
5እንደገናም በሰማርያ ኰረብቶች ላይ፣
 ወይን ትተክያለሽ፤
አትክልተኞች ይተክሏቸዋል፤
 በፍሬውም ደስ ይላቸዋል።
6ጠባቂዎች፣ በኤፍሬም ኰረብቶች ላይ፣
 ‘ኑ፤ ወደ ጽዮን፣

[*]3 ወይም እግዚአብሔር ከጥንት/ ከቀድሞ ተገለጠልን

30፥19 ዘፍ15፥5፤ 22፥17፤መዝ9፥2፤ 126፥1-2፤ኢሳ35፥10፤ 44፥23፤51፥11፤60፥9 ፤ኤር31፥4፤33፥22፤ ሕዝ37፥26፤ዘካ2፥4
30፥20 ዘፀ23፥22፤ ኢሳ54፥13፡14፤ኤር 31፥17፤ዘካ8፥5
30፥21 ቍ9፤ዘኍ 16፥5፤ዘዳ17፥15፤ኤር 23፥5-6
30፥22 ዘሌ26፥12፤ ኢሳ19፥25፤ሆሴ2፥23
30፥23 ኤር23፥19
30፥24 ኤር4፥8፡28 ፤23፥19-20፤ሰቆ1፥12
31፥1 ዘሌ26፥12
31፥2 ዘፀ33፥14፤ ዘኍ14፥20፤ዘዳ12፥9
31፥3 ዘዳ4፥37፤ሆሴ 11፥4፤ዮሐ6፥44
31፥4 ዘፍ31፥27፤ ዘፀ15፥20፤2ነገ19፥21 ፤ኤር1፥10፤30፥18፡19
31፥5 ዘዳ20፥6፤ኢሳ 37፥30፤ኤር33፥13፤ 50፥19፤አሞ9፥14፤ አብ1፥19
31፥6 ቍ12፤ዘዳ 33፥19፤ኢሳ52፥8፤ 56፥10፤ኤር50፥4-5፤ ሚክ 4፥2

30፥19 *የምስጋና መዝሙር፤* 33፥11 ይመ። *የእልልታ፤* 31፥4 እና ማብ ይመ፤ ከ15፥17 ጋር ያገናዝቡ። *አበዛቸዋለሁ … አይቀንስም፤* 29፥6፤ ሕዝ36፥37-38 ይመ። *አከብራቸዋለሁ … የተናቁም አይሆኑም፤* ኢሳ9፥1 ይመ።

30፥20 *እንደ ቀድሞው፤* ምናልባት የእስራኤል መንግሥት በሮብዓም ጊዜ ለሁለት ከመከፈሉ በፊት በተለይ በንጉሥ ዳዊት ዘመን እንደ ነበረው ሁኔታ ለማለት ይሆናል። *ማኅበረ ሰቡ፤* በ1ነገ12፥20 የተጠቀሰው ይህስ አስተዳደሩንና ሃይማኖት ነክ ጕዳዮችን የሚያቀናጅ ከሕዝቡ የተወጣጣ አካል ነው። *በፊቴ የጸና ይሆናል፤* መዝ102፥28፤ 2ሳሙ7፥24 ይመ።

30፥21 *መሪያቸው … ገዢቸውም፤* “ታርጕም” የተባለው የዕብራይስጡ የብሉይ ኪዳን የትርጓሜ መጽሐፍ በእነዚህ ቃላት ቦታ ‘መሲሕ’ የሚለውን ቃል ይጠቀማል፤ ይሁን እንጂ ቃላቱ የሚገልጡት ከምርኮ መልስ በኋላ ስለሚነሡት ስለ መጀመሪያዎቹ የይሁዳ አገር መሪዎች ይመስላል። ያም ሆኖ ይህ የትንቢቱ ፍጻሜ ራሱ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ነው። *ከራሳቸው ወገን … ከመካከላቸው ይነሣል፤* የሚገዛቸው ከባዕድ ወገን አይሆንም (ከዘዳ18፥15፡18 ጋር ያነጻጽሩ)። *አቀርበዋለሁ … ይቀርበኛል፤* ዘኍ16፥5 ይመ፤ ከዘፀ24፥2 ጋር ያገናዝቡ። ያለፈቃዱ እንዲሁ ወደ እግዚአብሔር መቅረብ በሞት ያስቀጣ ነበር (ዘፀ19፥21፤ ዘኍ8፥19 ይመ)።

*30፥22፤* 31፥1 ይመ፤ በተጨማሪም የ7፥23 ማብ ይመ።

*30፥23-24፤* በአብዛኛው ከ23፥19-20 ቃል በቃል የተወሰደ ነው (የዚያን ማብ ይመ)።

*31፥1-40፤* ኤርምያስ በዚህ ክፍል፣ በ30፥1 ላይ ስለ ጀመረው ለምርኮ የመመለስ ፍሬ ሐሳብ ከጌታ የተቀበለውን መልእክት (1)ለእግዚአብሔር ሕዝብ ሁሉ፣ ቍ1 (በስድ ንባብ)፤ (2)ለተመለሰው ለሰሜኑ የእስራኤል (ክፍል) ግዛት፣ ቍ2-22 (በግጥም)፤ (3)ከምርኮ ለተመለሰው ለደቡቡ የይሁዳ ግዛት፣ ቍ23-26 (በስድ ንባብ)፤ እንዲሁም (4)ለእስራኤልና ለይሁዳ በአንድነት፣ ቍ27-40 (መግቢያውን በስድ ንባብ፣ ቍ27-30፤ ሐተታውን በግጥም፣ ቍ27-37፤ መደምደሚያውን በስድ ንባብ፣ ቍ38-40 ጽፎት ይታያል፤ እያንዳንዱ ክፍል የሚዘጋው “ … ጊዜ ይመጣል” በሚል ሐረግ ነው)።

*31፥1፤* 30፥22 ይመ፤ በተጨማሪም የ7፥23 ማብ ይመ። *ለእስራኤል ነገድ ሁሉ፤* ለዐሥራ ሁለቱ ነገድ እስራኤል በሙሉ ማለት ነው።

31፥2 *ከሰይፍ የተረፈው ሕዝብ፤* ከምርኮ የሚመለሱትን የደጋጎቹን ሰዎች ቅሬታ ለማመልከት ነው (ቍ7 ይመ፤ በተጨማሪም የ6፥9 ማብ ይመ)። *በምድረ በዳ፤* የዐረብ ምድረ በዳ የሚያመለክት ሲሆን፣ እስራኤላውያን ከግብፅ ምድር ከወጡ በኋላ ከተጓዙበት የሲና በረሓ ጋር ይዛመዳል። ከምርኮ መመለስ ብዙውን ጊዜ ከግብፅ የባርነት አገዛዝ ነፃ ከመውጣት ጋር ተገናዝቦ ይታያል (16፥14-15 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ 35፥1-11 እና ማብ፤ 40፥3-4፤ 42፥14-16፤43፥18-21፤48፥20-21፤ 51፥9-11 ይመ፤ ከሆሴ2፥14-15 ጋር ያነጻጽሩ)። *ዕረፍት፤* 6፥16 ይመ፤ ከዘዳ28፥65 ጋር ያገናዝቡ። የዘዳ3፥20፤ የኢሱ1፥13 ማብ ይመ። *ለእስራኤል፤* የሰሜኑን መንግሥት የሚያመለክት ነው፤ ሰማርያ (ቍ5)፣ ኤፍሬም (ቍ6፡9፡18፡20)፣ ያዕቆብ (ቍ7፡11) እና ራሔል(ቍ15) በሚል መጠሪያም ይታወቃል።

31፥3 *በርኅራኄ ሳብሁሽ፤* መዝ36፥10 ላይ የዚሁ ሐሳብ ይገኛል፤ በተጨማሪም 6፥4 ማብ ይመ።

31፥4 *አንጽሻለሁ፤* 1፥10 እና ማብ ይመ። *የእስራኤል ድንግል፤* ቍ21፤ 18፥13 ይመ፤ በተጨማሪም 14፥17 እና ማብ ይመ። *ከበሮቹንም፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ከበሮ ለደስታ መግለጫ የሚውል የዜማ ዕቃ ነው (መዝ68፥15 ይመ)፤ በተለይም ሰራዊቱ ድልን ከተጐናጸፈ በኋላ በከበሮ የታጀበ ክብረ-በዓል ማዘጋጀት የተለመደ ነበር (ዘፀ15፥20 እና ማብ፤ መሳ11፥34 ይመ)፤ ይህ ሁሉ ከይሁዳ የምርኮ ዘመን መከራ አንጻር ሲታይ፣ ትልቅ ተስፋ የሚያሳድር ሆኖ ይገኛል (መዝ 137፥1-3 ይመ)። *ትፈነድቂያለሽ፤* ቍ13 ይመ፤ አደራረጉ በጥንት ዘመን የተለመደ ሃይማኖታዊ ሥርዐት ነበር (2ሳሙ6፥14 ይመ)። *ከሚፈነጥዙት፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ በ30፥19 ላይ “እልልታ” ተብሎ ተተርጕሞአል።

31፥5 *ትተክያለሽ፤* 1፥10 እና ማብ ይመ። *በሰማርያ፤* አሦራውያን ይህችን አገር ድል አድርገው የያዟት በ722-721 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነበር (2ነገ17፥24)፤ ዳግመኛም በእግዚአብሔር ሕዝብ እጅ ገብታ ተመልሰው ይኖሩባታል። *ይተክሏቸዋል፤ በፍሬውም ደስ ይላቸዋል፤* ዘዳ28፥30፤ ኢሳ62፥8-9፤ 65፥21-22 ይመ። ሕጉ አንድ ተክል ተተክሎ አምስት ዓመት ሳይሞላው ፍሬው አይበላ ብሎ ስለሚያዝ (ዘሌ19፥23-25 ይመ)፣ ወደ ተረጋጋ ሕይወት መመለሳቸው እዚህ ላይ ታስቦአል።

31፥6 *ጠባቂዎች በ … ኰረብቶች ላይ፤* ለምሳሌ፦ በኋለኞቹ ዘመናት፣ ጠባቂዎች በየጊዜው የሚለዋወጠውን የጨረ

ወደ አምላካችን ወደ እግዚአብሔር
እንውጣ!'
ብለው የሚጮኹበት ቀን ይመጣል::

[7]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

"ስለ ያዕቆብ በደስታ ዘምሩ፤
ስለ ሕዝቦች አለቃ እልል በሉ፤
ምስጋናችሁን አሰሙ፤
'እግዚአብሔር ሆይ፤ የእስራኤልን
ቅሬታ፣
ሕዝብህን አድን' በሉ::
[8]እነሆ፤ ከሰሜን ምድር አመጣቸዋለሁ፤
ከምድርም ዳርቻ እሰበስባቸዋለሁ፤
በመካከላቸውም ዕውሮችና አንካሶች፣
ነፍሰ ጡርና በምጥ ላይ ያሉ ሴቶች
ይገኛሉ፤
ታላቅም ሕዝብ ሆነው ይመለሳሉ::
[9]እያለቀሱ ይመጣሉ፤
እያጽናናሁ አመጣቸዋለሁ፤
እኔ ለእስራኤል አባት ነኝና፣
ኤፍሬም በኵር ልጄ ነውና፣
በውሃ ምንጭ ዳር፣
በማይሰናከሉበት ቀና መንገድ
እመራቸዋለሁ::

[10]"ሕዝቦች ሆይ፤ የእግዚአብሔርን
ቃል ስሙ፤
ሩቅ ባሉ የባሕር ጠረፎችም፣
'እስራኤልን የበተነ እርሱ ይሰበስበዋል፤
መንጋውንም እንደ እረኛ ይጠብቃል'
ብላችሁ ዐውጁ::

[11]እግዚአብሔር ያዕቆብን ይዋጀዋልና፤
ከእርሱም ከሚበረቱት እጅ ይታደገዋልና።
[12]መጥተውም በጽዮን ተራራ ላይ በደስታ
ይዘምራሉ፤
በእግዚአብሔርም ልግስና፣
በእህሉ፣ በወይን ጭማቂውና በዘይቱ፣
በፍየልና በበግ ጠቦት፣ በወይፈንና
በጊደር ደስ ይሰኛሉ፤
ውሃ እንደማይቋረጥባት የአትክልት ስፍራ
ይሆናሉ፤
ከእንግዲህም አያዝኑም::
[13]ኰረዶች ይዘፍናሉ፤ ደስም ይላቸዋል፤
ጕረምሶችና ሽማግሌዎችም ይፈነጥዛሉ፤
ልቅሶአቸውን ወደ ደስታ እለውጣለሁ፤
ከሐዘናቸውም አጽናናቸዋለሁ፤ ደስታንም
እሰጣቸዋለሁ::
[14]ካህናቱን አትረፍርፌ እባርካለሁ፤
ሕዝቤም በልግስናዬ ይጠግባል፤"
ይላል እግዚአብሔር::

[15]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

"ዋይታና መራራ ልቅሶ፣
ከራማ ተሰማ፤
ልጆቿ የሉምና፣
ራሔል አለቀሰች፤
መጽናናትም እንቢ አለች::"

[16]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

"ድምፅሽን ከልቅሶ፣
ዐይኖችሽንም ከእንባ ከልክይ፤
ድካምሽ ያለ ዋጋ አይቀርምና፤"

31፥7 ዘዳ28፥13፤ መዝ14፥7፤28፥9፤ኢሳ 12፥6፤37፥31፤61፥9
31፥8 ዘፍ33፥13፤ ዘዳ30፥4፤መዝ106፥ 47፤ኢሳ42፥16፤ኤር 3፥18፤ሕዝ34፥12-14፤ 16፤ሚክ4፥6
31፥9 ዘፀ4፥22፤ ዘኍ20፥8፤ዕዝ3፥12፤ መዝ1፥3፤126፥5፤ኢሳ 32፥2፤40፥4፤49፥11፤ 63፥13፤ኤር3፥4
31፥10 ዘሌ26፥33፤ ዘዳ30፥4፤ኢሳ11፥12፤ 40፥11፤49፥1፤66፥19 ፤ኤር25፥22፤50፥19፤ ሕዝ34፥12
31፥11 ዘፀ6፥6፤ መዝ142፥6፤ዘካ9፥16
31፥12 ቍ24፤ዘኍ 18፥12፤መዝ36፥8፤12 6፥5፤መሓ4፥15፤ኢሳ 30፥19፤62፥5፤65፥10 ፤ሕዝ17፥23፤20፥40፤ 40፥2፤ሆሴ2፥21-22፤ ኢዩ2፥19፤3፥18፤ሚክ 4፥1፤ዮሐ16፥22፤ራእ 7፥17
31፥13 መዝ30፥11 ፤ኢሳ40፥1፤51፥11፤ 61፥3
31፥14 ቍ25፤ዘሌ 7፥35-36፤መዝ36፥8፤ ኢሳ30፥23
31፥15 ዘፍ37፥35፤ ኢሱ18፥25፤ኤር10፥ 20፤ማቴ2፥17-18
31፥16 ሩት2፥12፤ 2ዜና15፥7፤መዝ30፥5 ፤ኢሳ25፥8፤30፥19፤ ኤር30፥3፤ሕዝ11፥17

ቃን መልክ (ገጽታ) ተመልክተው ታላላቅ በዓላት የሚውሉባቸውን ዕለታት ለይተው ለመወሰን ይችሉ ዘንድ (ዘዳ16፥16)፤ አመቺ በሆነና ከፍታ ባለው ቦታ ላይ ተመድበው ይጠባበቁ ነበር:: *በኤፍሬም ... ወደ ጽዮን*፣ በቀዳማዊ ኢዮርብዓም ዘመን የሰሜኑ መንግሥት ሕዝብ፣ በሰሜኑ የመስገጃ ስፍራዎች እየተገኙ ሥርዐተ አምልኮን የመፈጸም ግዴታ ነበረባቸው (1ነገ 12፥26-30):: ወደ ፊት ግን እግዚአብሔርን ብቻ በኢየሩሳሌም ያመልኩታል (ከዮሐ4፥20 ጋር ያነጻጽሩ):: *እንውጣ* ይህ ግሥ ብዙውን ጊዜ በዙሪያዋ ካሉት ቦታዎች ተለይታ ጕብ ወዳለችው ወደ ኢየሩሳሌም የሚደረገውን ጕዞ የሚያሳይ ነው (ለምሳሌ:- ዕዝ1፥3፤ 7፥7፤ ኢሳ2፥3 ይመ)::

31፥7 *ስለ ሕዝቦች አለቃ፤* ዘዳ26፥19፤ አሞ6፥1 ይመ:: እስራኤል ከሌሎቹ ይልቅ ታላቅ መንግሥት ነበረች፤ ይህንን ታላቅነት ያገኘችውም፣ ከራሷ ጥረት፣ ትጋትና ብርታት የተነሣ ሳይሆን፣ በእግዚአብሔር ጸጋና ምርጫ ነው(ዘዳ7፥6-8፤ 2ሳሙ 7፥23-24 ይመ):: *አድን*፤ "ሆሣዕና" ለሚለው ቃል በዕብራይስጥ መሠረቱ ወይም መገኛው ይህ ቃል ነው:: ቃሉ፣ በወንጌል ተጽፎ እንደምናገኘው፣ ሕዝቡ በሆሣዕና እሑድ ድምፃቸውን ከፍ አድርገው ማሰማታቸውን ያስታውሰናል (ማቴ21፥9 ይመ፤ በተጨማሪም መዝ20፥9፤28፥9፤86፥2፤ በተለይም መዝ118፥25 ይመ):: *ቅሬታ፤* የ6፥9 ማብ ይመ::

31፥8 *ከሰሜን ምድር*፤ 3፥18 እና ማብ፤ 4፥6 እና ማብ፤ 6፥22፤16፥15 ይመ:: *ከምድርም ዳርቻ*፤ 6፥22፤25፥32 ይመ:: *ዕውሮችና አንካሶች*፤ ኢሳ35፥5-6 እና ማብ፤ 42፥16 ይመ::

31፥9 *እያለቀሱ፤* ከመዝ126፥5-6፤ ከኢሳ55፥12 ጋር ያገናዝቡ:: *እመራቸዋለሁ፤* ኢሳ40፥11፤ 48፥21 ይመ፤ ከኢሳ20፥4 ጋር ያገናዝቡ:: *በውሃ ምንጭ ዳር፤* ኢሳ49፥10 ይመ፤ እንዲሁም 41፥18 ይመ:: *ቀና መንገድ፤* ኢሳ40፥3-4 እና ማብ፤ 43፥16:19 ይመ:: *እኔ ለእስራኤል አባት ነኝና፤* 3፥4 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዘዳ32፥6፤ ኢሳ63፥16፤ 64፥8 ይመ:: *በኵር ልጄ*፤ ከቍ20 ጋር ያነጻጽሩ፤ ዘፀ4፥22 እና ማብ፤ ሆሴ11፥1-4 ይመ::

31፥10 *ሩቅ ባሉ የባሕር ጠረፎችም*፤ ከእስራኤል ምድር በስተ ምዕራብ በኩል የሚገኙ ቦታዎች ናቸው (2፥10፤ 25፥22 እና ማብ፤ 47፥4፤ መዝ72፥10፤ ኢሳ41፥1:5፤ 42፥10:12፤ 49፥1 ይመ):: *እስራኤልን የበተነ ... መንጋውንም እንደ እረኛ ይጠብቃል*፤ 23፥1-3 እና ማብ ይመ::

31፥11 *ይታደገዋልና*፤ የሩት 2፥20 ማብ ይመ:: እግዚአብሔር ሕዝቡን ከግብፅ ባርነት እንዳወጣ (ዘፀ6፥6፤ 15፥13፤ ዘዳ 7፥8፤ 9፥26 ይመ)፤ አሁንም ደግሞ ዘራቸውን ከባቢሎን ምርኮ ይታደጋል (ኢሳ 41፥14 እና ማብ፤ 43፥1 እና ማብ፤ 52፥9 ይመ):: *ከእርሱም ከሚበረቱት ...፤* መዝ35፥10 ይመ::

31፥12 *በጽዮን ተራራ፤* የ17፥12 ማብ ይመ:: *በእግዚአብሔር ልግስና*፤ ምድራዊውን በረከት ያመለክታል (ቍ14፤ ሆሴ3፥5 ይመ):: *በእህሉ፣ በወይን ጭማቂውና በዘይቱ*፤ የዘዳ 7፥13 ማብ ይመ:: በተጨማሪም ሆሴ2፥8 ይመ:: *ውሃ እንደ ማይቋረጥባት የአትክልት ስፍራ፤* ኢሳ58፥11 እና ማብ ይመ:: *ከእንግዲህም ... አያዝኑም*፤ የኢሳ25፥8 ማብ ይመ::

31፥14 *አትረፍርፌ*፤ ይህ ማለት (1)የእግዚአብሔር ልግስና ተመሳሳይ (መዝ36፥8፤ 63፥5፤ ኢሳ55፥2 ይመ)፤ ወይም (2)ለካህናት ልዩ ድርሻ ሆነው የሚቀርቡትን የመሥዋዕት እንስሳት የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ዘሌ7፥31-36 ይመ)::

*31፥15፤* ሄሮድስ፣ በቤተ ልሔምና በዙሪያዋ "ያሳረዳቸውን ወንዶች ሕፃናት" አስመልክቶ፣ ይህ ትንቢት መፈጸሙን (ማቴ 2፥16-18 ይመ) ማቴዎስ ጠቅሶ በወንጌሉ ጽፎታል:: *ራማ፤* ከኢየሩሳሌም ከተማ ነዋሪዎች ተማርከው ወደ ባቢሎን በሄዱ ጊዜ እግረ መንገዳቸውን ካለፉባቸው ከተሞች አንዷ ናት (40፥1 ይመ፤ ከኢሳ10፥29፤ ከሆሴ5፥8 ጋር ያነጻጽሩ):: *ራሔል*፤ የያዕቆብ ተወዳጅ ሚስት ናት (ዘፍ 29፥30 ይመ)፤ በሰሜኑ የእስራኤል ግዛት ዝነኛና ኀያላን የሆኑት ነገዶች ኤፍሬምና ምናሴ ከልጇ ከዮሴፍ የተወለዱ ናቸው (ዘፍ30፥22-24፤ 48፥1-2 ይመ):: ስሟ እዚህ ላይ መነሣቱ የሰሜኑን ግዛት በሰውኛ ዘይቤ ለመግለጽ ነው (የቍ2 ማብ ይመ)::

31፥16 *ድካምሽ ያለ ዋጋ አይቀርምና*፤ ይህ ሐሳብ በ2ዜና 15፥7 ላይ ተንጸባርቆአል:: እዚህ ላይ የተጠቀሰው ድካም ልጆችን መውለድና ማሳደግን የሚያመለክት ነው::

ይላል እግዚአብሔር።
"ከጠላት ምድር ይመለሳሉ፤
[17]ስለዚህ ወደ ፊት ተስፋ አለሽ"
ይላል እግዚአብሔር።
"ልጆችሽ ወደ ገዛ ምድራቸው
ይመለሳሉ።

[18]"የኤፍሬምን የሲቃ እንጕርጕሮ በእርግጥ
ሰምቻለሁ፤
'እንዳልተገራ ወይፈን ቀጣኸኝ፤
እኔም ተቀጣሁ።
አንተ እግዚአብሔር አምላኬ ነህና፣
መልሰኝ፤ እኔም እመለሳለሁ።
[19]ከአንተ ከራቅሁ በኋላ፣
ተመልሼ ተጸጸትሁ፤
ባስተዋልሁም ጊዜ፣
ጭኔን መታሁ፣
የወጣትነት ውርደቴን ተሸክሜአለሁና፣
ዐፈርሁ፤ ቀለልሁም።'
[20]ኤፍሬም የምወደው፣
ደስም የምሰኝበት ልጄ አይደለምን?
ብዙ ጊዜ ተቃውሜው ብናገርም፣
መልሼ ስለ እርሱ አስባለሁ፤
አንጀቴ ይላወሳል፤
በታላቅ ርኅራኄም እራራለታለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር።

[21]"የጕዳና ምልክት አቁሚ፤
መንገድ አመልካች ትከዪ፤
የምትሄጂበትን መንገድ፣
አውራ ጐዳናውን አስተውዪ፤
ድንግሊቱ እስራኤል ሆይ፤ ተመለሺ፤
ወደ ከተሞችሽም ግቢ።
[22]አንቺ ከዳተኛ ልጅ ሆይ፤
እስከ መቼ ትቅበዘበዥለሽ?
እግዚአብሔር በምድር ላይ አዲስ ነገር
ይፈጥራል፤
ሴት በወንድ ላይ ከበባ ታደርጋለች።[ሀ]

[23]የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚ አብሔር እንዲህ ይላል፤ "ምርኮአቸውን በመለስሁላቸው ጊዜ፣[ለ] እነርሱ በይሁዳ ምድርና በከተሞቿ፣ 'አንተ የጽድቅ ማደ ሪያ ቅዱስ ተራራ ሆይ፤ እግዚአብሔር ይባ ርክህ!' የሚል አነጋገር እንደ ገና ይጠቀማ ሉ። [24]ገበሬዎችና ዘላን ከብት አርቢዎች በይሁዳና በከተሞቿ በአንድነት ይኖራሉ። [25]የዛለችውን ነፍስ ዐድሳለሁ፤ የደከመችው ንም አበረታለሁ።"

[26]በዚህ ጊዜ ከእንቅልፌ ነቅቼ ዙሪያዬን ተመለከትሁ፤ እንቅልፌም ጣፋጭ ሆኖልኝ ነበር።

[27]"እነሆ፤ የእስራኤልን ቤትና የይሁዳን ቤት" ይላል እግዚአብሔር፤ "በሰውና በእን ስሳት ዘር የምሞላበት ጊዜ ይመጣል፤ [28]ል ነቅላቸውና ላፈርሳቸው፣ ልገለብጣቸውና ላጠፋቸው፣ መከራም ላመጣባቸው እንደ ተጋሁ ሁሉ፣ ላንጻቸውና ልተክላቸው ደግሞ እተጋለሁ" ይላል እግዚአብሔር።

[29]"በዚያ ዘመን ሰዎች ዳግመኛ፣
'አባቶች በበሉት ጎምዛዛ የወይን ፍሬ፣
የልጆች ጥርስ ጠረሰ' የሚለውን ምሳሌ
አይናገሩም።

[30]ነገር ግን፣ እያንዳንዱ በገዛ ኀጢአቱ ይሞታል፤ ጎምዛዛ የወይን ፍሬ የሚበላ ሁሉ የራሱ ጥርስ ይጠርሳል።

[31]"ከእስራኤል ቤትና፣

31፥17 ኢዮ8፥7፤ ኤር30፥20፤ሰቆ3፥29
31፥18 ኢዮ5፥17፤ መዝ80፥3፤ኤር50፥11 ፤ሆሴ4፥16፤10፥11
31፥19 ዕዝ9፥6፤ መዝ25፥7፤95፥10፤ ኤር8፥4፤22፥21፤ሕዝ 36፥31፤21፥12፤ሉቃ 18፥13
31፥20 1ነገ3፥26፤ መዝ6፥2፤ኢሳ44፥21፤ 55፥7፤ሰቆ3፥33፤ሚክ 7፥18
31፥21 ቊ4፤ኢሳ 35፥8፤52፥11፤ኤር3፥ 12፤50፥5፤ሕዝ21፥19
31፥22 ዘዳ32፥10፤ ኢሳ43፥19፤ኤር2፥23 ፤3፥6
31፥23 ዘፍ28፥3፤ ዘኍ6፥24፤መዝ 48፥1፤ኢሳ1፥26፤2፥2፤ ኤር30፥18
31፥24 ቊ12፤ኤር 30፥18፤ዘካ8፥4-8
31፥25 ኢሳ40፥29፤ ዮሐ4፥14
31፥26 ዘካ4፥1
31፥27 ኤር16፥14፤ ሆሴ2፥23
31፥28 ኢዮ29፥2፤ ዘዳ28፥63፤29፥28፤ 30፥9፤ኤር1፥10፤18፥ 8፤ሕዝ36፥10-11፤ አሞ9፥14
31፥29 ዘፍ9፥25፤ ዘዳ24፥16፤ሰቆ5፥7፤ ሕዝ18፥2
31፥30 2ነገ14፥6፤ ኢሳ3፥11፤ገላ 6፥7
31፥31 ዘዳ29፥14፤ ኢሳ42፥6፤54፥10፤ ሉቃ22፥20፤ዕብ 8፥8-12፤10፥16-17

[ሀ]22 *ወይም መፈለግ ትጀምራለች ወይም መጠበቅ ትጀምራለች*
[ለ]23 *ወይም ዕድል ፈንታቸውን በመለስሁላቸው*

31፥17 *ወደ ፊት ተስፋ፤* 29፥11 ይመ። *ልጆችሽ ... ይመለሳሉ፤* ከሆሴ 11፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ።

31፥18-19 *መልሰኝ ... እመለሳለሁ ... ከራቅሁ፤* በዕብራ ይስጡ ሦስቱም ቃላት የተገኙት ከአንድ ሥርወ ቃል ነው (8፥4-5 እና ማብ ይመ)።

31፥18 *እንዳልተገራ ወይፈን፤* በሆሴ4፥16፤ 10፥11 ላይም ይህ አባባል ገብቶ ይገኛል።

31፥19 *ጭኔን መታሁ፤* የሐዘንና የትካዜ ምልክት ነው (ሕዝ 21፥12 ይመ)። *ዐፈርሁ፤ ቀለልሁም፤* ኢሳ45፥16 ይመ። *የወጣት ነት፤* የመጀመሪያውን ጊዜ ታሪክ ለማለት ነው (2፥2፤ 3፥24-25፤ 22፥21፤ 32፥30፤ ኢሳ54፥4፤ ሕዝ16፥22 ይመ)።

31፥20 *ደስም የምሰኝበት ልጄ፤* ከኢሳ5፥7 ጋር ያነጻጽሩ። *ብዙ ጊዜ ... ብናገርም... በታላቅ ርኅራኄም እራራለታለሁ፤* ሆሴ11፥1-4፡8-9 ይመ። *አንጀቴ ይላወሳል፤* ኢሳ16፥11 ይመ።

*31፥21፤* በምርኮ የተጋዙት ሰዎች፣ ወቅቱ ደርሶ ወደ ይሁ ዳ ምድር በሚመለሱበት ጊዜ፣ መንገድ እንዳይጠፋቸው ከአሁኑ ምልክት እንዲያቆሙ እየተመከሩ ነው። *የጕዳና ምልክት፤* ትክል ድንጋይ ማለት ነው (2ነገ23፥17፤ ሕዝ39፥15 ይመ)። *ድንግሊቱ እስራኤል፤* ቊ4 ይመ፤ በተጨማሪም 14፥17 እና ማብ ይመ።

31፥22 *አንቺ ከዳተኛ ልጅ፤* የይሁዳ ሕዝብ ከሓዲ ነበር (3፥14፡22 ይመ)። *አዲስ ነገር ይፈጥራል፤* ኢሳ42፥9 እና ማብ ይመ። *ከበባ፤* ቃሉ በርኅራኄና በጽኑ ፍቅር ዐቅፎ መያዝን ያመ ለክታል (መዝ32፥7፡10 ይመ፤ በተጨማሪም መዝ26፥6 ይመ)። ይሁዳ አንድ ቀን ተመልሳ እግዚአብሔርን በሙሉ ልቧ ትወዳ ለች።

31፥23 *ምርኮአቸውን በመለስሁላቸው ጊዜ፤* የ29፥14 ማብ ይመ። *እግዚአብሔር ይባርክህ፤* መዝ128፥5፤ 134፥3 ይመ። *የጽድቅ ማደሪያ፤* ኢየሩሳሌምን ማለት ነው (ከኢሳ 1፥21፡26 ጋር ያነጻ ጽሩ)። *ቅዱስ ተራራ፤* ቤተ መቅደሱ የነበረበት ተራራ ነው (መዝ2፥6፤ 48፥1-2፤ ኢሳ2፥2-3፤ 11፥9፤ 27፥13፤66፥20 ይመ)።

31፥26 *ነቅቼ፤* ኤርምያስ ቀደም ሲል የተሰጠውን መለኮ ታዊ መገለጥ ያገኘው (ከ30፥3 ጀምሮ ያለውን) ያስገኘው በሕ ልም እንደ ነበር ግልጽ ነው (ለተመሳሳይ ሁናቴ ዳን 10፥9፤ ዘካ 4፥1 ይመ)። *እንቅልፌም ጣፋጭ፤* ምሳ3፥24 ይመ።

31፥27 *ዘር የምሞላበት ...፤* ሕዝ36፥8-11 ይመ። በዕብራ ይስጡ የሁለቱም ቃላት ሥርው አንድ ነው። *የእስራኤልን ... የይሁዳን፤* ሰሜንና ደቡብ እንደ ገና አንድ ይሆናሉ ማለት ነው (3፥18 እና ማብ ይመ)።

31፥28 *እንደ ተጋሁ ... እተጋለሁ፤* የ1፥12 ማብ ይመ። *ልነቅላቸውና ላፈርሳቸው፣ ልገለብጣቸውና ላጠፋቸው ... ላንጻ ቸውና ልተክላቸው፤* የ1፥10 ማብ ይመ።

31፥29 *አባቶች ... ጠረሰ፤* ሕዝ18፥2 ላይ ድጋሚ ተጽፎ አል። ይህ አባባል በዘፀ20፥5 እና በዘኍ14፥18 ላይ አንድ ሰው የሠ ራው ኀጢአት፣ በልጆቹና በልጅ ልጆቹ ላይ አሉታዊ ተጽዕኖ ሊያ መጣ ይችላል ተብሎ የተሰጠውን ትምህርት በውል ካለመረዳት የተነሣ የተጠቀሰ ምሳሌያዊ አነጋገር ይመስላል። በኤርምያስና በሕዝቅኤል ዘመን የነበሩ ሰዎች ከእግዚአብሔር የሚወርድባቸው የቅጣት በትር በራሳቸው ኀጢአት ሳይሆን፣ በቀድሞ አባቶቻቸው በደል ምክንያት የመጣ መሆኑን ያምኑ ነበር።

31፥30 *እያንዳንዱ በገዛ ኀጢአቱ ይሞታል፤* ዘዳ24፥16፤ሕዝ 18፥3፡20፤ 33፥7-18 ይመ። የቡድን ወይም የወል ኀላፊነት መኖሩ ጠቃሚ ቢሆንም ሕዝቡ ኀላፊነቱን በቀድሞ አባቶች ላይ ቢላከክም፣ ኤርምያስና ሕዝቅኤል በኢየሩሳሌም በቅርቡ በሚደር ስባት ጥፋት የግል ኀላፊነትና ተጠያቂነት እንዳለም አበክረው አስገንዝበዋል።

*31፥31-34፤* ይህ ክፍል ከኤርምያስ ትንቢቶች ሁሉ ሁነኛ

ከይሁዳ ቤት ጋር" ይላል እግዚአብሔር፤
"አዲስ ቃል ኪዳን የምገባበት፣
ጊዜ ይመጣል።
[32]ከግብፅ አወጣቸው ዘንድ፣
እጃቸውን ይዤ በመራኋቸው ጊዜ፣
ከአባቶቻቸው ጋር እንደገባሁት ኪዳን
አይደለም፤[x]
የእነርሱ ባል[1] ሆኜ ሳለሁ፣
ቃል ኪዳኔን አፍርሰዋልና።"
ይላል እግዚአብሔር።
[33]"ነገር ግን ከዚያ ጊዜ በኋላ፣
ከእስራኤል ቤት ጋር የምገባው ኪዳን
ይህ ነው" ይላል እግዚአብሔር፤
"ሕጌን በልቡናቸው አኖራለሁ፤
በልባቸውም እጽፈዋለሁ።
እኔ አምላክ እሆናቸዋለሁ፤
እነርሱም ሕዝቤ ይሆናሉ።
[34]ከእንግዲህ ማንም ሰው ባልንጀራውን፣
ወይም ወንድሙን፣ 'እግዚአብሔርን
ዕወቅ' ብሎ አያስተምርም፤
ከትንሹ ጀምሮ እስከ ትልቁ፣
ሁሉም እኔን ያውቁኛልና፤"
ይላል እግዚአብሔር።
"በደላቸውን ይቅር እላለሁ፤
ኀጢአታቸውንም መልሼ አላስብም።"
[35]በቀን እንድታበራ፣
ፀሐይን የመደበ፣
በሌሊት እንዲያበሩ፣
ጨረቃንና ከዋክብትን ያዘዛቸው፣
የሞገዱ ድምፅ እንዲተምም፣
ባሕሩን የሚያናውጥ፣
ስሙ የሰራዊት ጌታ የሆነ፣
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
[36]"ይህ ሥርዐት በፊቴ ከተሻረ፣"
ይላል እግዚአብሔር፤
"በዚያ ጊዜ የእስራኤልም ዘር በፊቴ፣
መንግሥት መሆኑ ለዘላለም ይቀራል።"
[37]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"በላይ ያሉትን ሰማያትን መለካት፣
በታችም ያሉትን የምድር መሠረቶች
መመርመር ከተቻለ፣
በዚያ ጊዜ የእስራኤልን ዘር ሁሉ፣
ስላደረጉት ነገር ሁሉ እጥላቸዋለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር።

[38]"እነሆ ከሐናንኤል ግንብ ጀምሮ እስከ ማእዘኑ በር ድረስ" ይላል እግዚአብሔር፤ "ይህች ከተማ ለእግዚአብሔር የምትሠራበት ጊዜ ይመጣል፤ [39]መለኪያ ገመዱም ከዚያ ጀምሮ በቀጥታ ወደ ጋሬብ ኰረብታ፣ በል ፎም ወደ ጎዓ ይዘረጋል። [40]ሬሳና ዐመድ የሚጣልበት ሸለቆ በሙሉ፣ በምሥራቅ በኩል

31፥32 ዘፀ24፥8፤ ዘዳ5፥3፤ ኤር11፥4
31፥33 ዘፀ4፥15፤ ዘዳ6፥6፤ ኤር 11፥4፤ 2ቆሮ3፥3፤ ዕብ10፥16
31፥34 ኢዮ7፥21፤ ኢሳ11፥9፤38፥17፤ መዝ85፥2፤130፥4፤ ኤር33፥8፤50፥20፤ ሚክ7፥19፤ዮሐ6፥45፤ ዕብ10፥17፤1ዮሐ2፥27
31፥35 ዘፍ1፥16፤ ዘፀ14፥21፤መዝ93፥3፤ 136፥7-9፤ኤር10፥16
31፥36 ኢዮ38፥33፤ መዝ89፥36-37፤ኤር 33፥20-26
31፥37 ኢዮ38፥5፤ ኤር33፥22፡24-26፤ ሮሜ11፥1-5
31፥38 2ነገ14፥13፤ 2ዜና25፥23፤ነህ3፥1፤ ኤር30፥18
31፥39 1ነገ7፥23
31፥40 2ሳሙ15፥23፤2ነገ11፥16፤ኢሳ 4፥3፤ኤር2፥23፤7፥31-32፤8፥2፤ኢዩ3፥17፤ ዘካ14፥21፤ዮሐ18፥1

[x]32 የዕብራይስጡ፣ የሰብዓ ሊቃናትና የሱርስት ትርጕሞች *እኔም ዘወር አልሁባቸው* ይላሉ።
[1]32 *ወይም የእነርሱ ጌታ*

ስፍራ የሚሰጠው፣ ዐይነተኛ ትንቢት ነው፤ የአዲስ ኪዳን ጸሐፊዎች ከብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ከጠቀሱአቸው ሁሉ በርዝመቱና የክፍሉ ፍሬ ሐሳብ ሳያቋርጥ በተከታታይ በመጠቀሱ አንደኛ ነው (የዕብ8፥8-12 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዕብ10፥16-17 ይመ)። በቍ31 ላይ፣ በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት እዚህ ላይ ብቻ የሚገኘውን "አዲስ ኪዳን" የሚለውን ሐረግ እንመለከታለን፤ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደዚህች ምድር ከመጣ በኋላ የተጻፈውንና "አዲስ ኪዳን" የተሰኘው የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል ስያሜ የተገኘው ከዚህ ነው።

31፥31 *ጊዜ ይመጣል፤* ዕብራይስጡ ቃል በቃል ከተተረጐመ፣ "ዘመን ይመጣል" የሚል ይሆናል (ቍ27፡38 ላይ ተመሳሳይ ሐረግ አለ)፤ ሐረጉ የመሢሑን ዘመን ያመለክታል። *የምገባበት፤* ዕብራይስጡ ቃል በቃል ሲተረጐም "የምቈርጥበት" የሚል ትርጕም ይሿል (የ34፥18፤ የዘፍ15፥18 ማብ ይመ)። *አዲስ ኪዳን፤* በቍ31-34 ላይ የተሰጠውን ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 1ቆሮ11፥25፤ 2ቆሮ3፥6፤ ዕብ9፥15፤ 12፥24 ይመ። ብሉይ ኪዳን በሚሠዉት እንስሳት ደም ይከበርና ይጸና እንደ ነበር፣ አዲስ ኪዳንም በኢየሱስ ክርስቶስ ደም ጸንቶአል፤ ከብሮአልም። *ከእስራኤል ቤትና ከይሁዳ ቤት፤* እንደ ገና የተዋሐደው የእግዚአብሔር ሕዝብ ማለት ነው (3፥18 እና ማብ ይመ)።

31፥32 *ከአባቶቻቸው ጋር እንደ ገባሁት ኪዳን፤* 7፥23፤ 11፥1-8፤ ዘዳ19፥5፤ 20፥22-23፥19 እና ማብ ይመ። በሲና የተሰጠው ኪዳን ኋላ "ብሉይ ኪዳን" በመባል ታወቀ (2ቆሮ 3፥14)፤ ወይም "የቀድሞው ኪዳን" ተብሎ ተጠራ (ዕብ8፥7፤ 9፥15፡18)። *እጃቸውን ይዤ በመራኋቸው ጊዜ፤* ሆሴ11፥3-4 ይመ። *ኪዳኔን አፍርሰዋልና፤* 11፥10 ይመ፤ የእግዚአብሔር ኪዳን ለመጣሱ ምክንያት የሆኑት ሕዝቡ ናቸው እንጂ እግዚአብሔር አይደለም (የኢሳ 24፥5 ማብ ይመ)። *ባል ሆኜ ሳለሁ፤* 3፥14 እና ማብ ይመ።

31፥33 *ከእስራኤል ቤት፤* እዚህ ላይ የእስራኤልንና የይሁዳን አንድነት የሚያመለክት አባባል ነው (ቍ31 እና የ3፥18 ማብ ይመ)። *ሕጌን በልቡናቸው አኖራለሁ፤* በውስጣቸው ለማለት ነው (ዘዳ6፥6፤ 11፥18፤ 30፥14፤ ሕዝ11፥19፤ 18፥31፤ 36፥26-27 ይመ)፤ ይኸውም በውጭ ከማስቀመጥ ጋር የሚነጻጸር ነው (9፥13፤ ዘዳ4፥8፤ 11፥32 ይመ)። *በልባቸውም እጽፈዋለሁ፤* ሕይወታቸውን በሚገባ እንዲመራና እንዲገዛ ማለት ነው፤ በድንጋይ ላይ ጽፎ ማቅረቡ ውጤታማ አለመሆኑን በንጽጽር መልክ ለማሳየት ነው (ዘፀ24፥4፤ 31፥18፤ 32፥15-16፤ 34፥28-29፤ ዘዳ4፥13፤ 5፥22፤ 9፥9፡11፤ 10፥4 ይመ)። *እኔ አምላክ ... ሕዝቤ ይሆናሉ፤* የ7፥23 ማብ ይመ። "አዲሱ" ኪዳን "አሮጌውን" ኪዳን አይሽረውም፤ ነገር ግን አሮጌው እንዲፈጸምና ዐላማው ግቡን እንዲመታም ይተካዋል።

31፥34 *ከእንግዲህ ... ባልንጀራውን ... አያስተምርም፤* እግዚአብሔር አዲሱን ሥራውን በሚያከናውንበት ጊዜ፣ ስለ እርሱም ሆነ ለሰዎች ስላለው ፈቃድ የሚያውቁ በሕዝቡ መካከል አይገኙም። እውነተኛ የሆነ እግዚአብሔርን የማወቅ መንፈስ በሁሉም ዘንድ ይኖራል፤ ወጣትም ሆነ ሽማግሌ፣ ተራውም ሆነ ባለሥልጣኑ እኩል እግዚአብሔርን ያውቁታል (5፥4-5) እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 32፥38-40፤ ኢሳ54፥13 እና ማብ፤ ሕዝ11፥19-20፤ 36፥25-27፤ ኤፌ3፥12፤ዕብ 4፥16፤ 10፥19-22 ይመ)። *ዕወቅ፤* በሕይወት ልምምድ ማወቅን እንጂ በቃላት ብቻ የሚነገር የአእምሮ ዕውቀትን የሚያመለክት አይደለም (ዘፀ6፥3 እና ማብ ይመ)። *በደላቸውን ይቅር እላለሁ፤ ኀጢአታቸውንም ...፤* የአዲሱን ኪዳን መሠረት የሚያጐላ ነው (ዕብ10፥14-17 ይመ)።

31፥35 *ፀሐይን የመደበ ... ጨረቃንና ከዋክብትን ያዘዛቸው፤* ዘፍ1፥16-18 እና ማብ ይመ። *የሚያናውጥ፣ ስሙ ... የሆነ፤* በኢሳ51፥15 ላይ ተመሳሳይ ስንኝ ይገኛል (መዝ 46፥3፤ ኢሳ17፥12 ይመ)።

*31፥36፤* 33፥20-21፡25-26 ይመ። የእግዚአብሔር የሥነ ፍጥረቱ ሕግና ሥርዐት የጸና መሠረት እንዳለው ሁሉ፣ እስራኤልም እንዲሁ ሁልጊዜ ዘር ይኖራታል።

31፥37 *ሁሉ እጥላቸዋለሁ፤* የይሁዳን መንግሥት እስፈሪ ፍርድ ጠራርጐ ሊያጠፋው የተቃረበ ቢሆንም፣ እስራኤል ግን ጸንታ ትኖራለች።

*31፥38-40፤* ዘካ14፥10-11 ይመ።

31፥38 *ይህች ከተማ፤* ኢየሩሳሌምን ነው። *ከሐናንኤል ግንብ ... ማእዘኑ በር፤* የሰሜኑ ቅጥር ምሥራቃዊና ምዕራባዊ ጫፍ ማለት ነው (የዘካ14፥10 ማብ ይመ)።

31፥39 *መለኪያ ገመዱም፤* በሕዝ40፥3፤ ዘካ1፥16፤ 2፥1 ላይም ከኢየሩሳሌም ተመልሶ መገንባት ጋር ተያይዞ ተጠቅሶአል። *ጋሬብ ... ጎዓ፤* እነዚህ ኰረብቶች ምናልባት ከኢየሩሳሌም በስተ ምዕራብ የሚገኙ ሳይሆኑ አልቀሩም።

31፥40 *ሸለቆ፤* ምናልባት የሄኖም ሸለቆ ሳይሆን አይቀርም

የቄድሮንን ሸለቆ ይዞ እስከ ፈረስ በር የሚደርሰው ደልዳላ ቦታ ሁሉ *ለእግዚአብሔር* የተቀደሰ ይሆናል፤ ከእንግዲህም ከተማይቱ አትነቀልም፤ አትፈርስምም።"

## ኤርምያስ የዕርሻ ቦታ መግዛቱ

**32** የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ በነገሠ በዐሥረኛው ዓመት፣ ይኸውም በባቢሎን ንጉሥ በናቡከደነፆር ዐሥራ ስምንተኛ ዘመነ መንግሥት፣ ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ ኤርምያስ የመጣው ቃል ይህ ነው፤ [2]በዚያን ጊዜም የባቢሎን ንጉሥ ሰራዊት ኢየሩሳሌምን ከቦ ነበር፤ ነቢዩ ኤርምያስም በይሁዳ ንጉሥ ቤተ መንግሥት በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ ተዘግቶበት ነበር።

[3]የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስም እንዲህ በማለት አሳስሮት ነበር፤ "እንዴት እንደዚህ ያለ ትንቢት ትናገራለህ? '*እግዚአብሔር*፤ "ይህችን ከተማ ለባቢሎን ንጉሥ አሳልፌ እሰጣታለሁ፤ እርሱም ይይዛታል። [4]የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስም ለባቢሎን ንጉሥ ዐልፎ ይሰጣል፤ ፊት ለፊትም ያነጋግረዋል፤ በዐይኖቹም ያየዋል እንጂ ከባቢሎናውያን[ሠ] እጅ አያመልጥም። [5]ሴዴቅያስንም ወደ ባቢሎን ይወስደዋል፤ በፍርዴ እስከምጐበኘውም ድረስ በዚያ ይቈያል፤ ይላል *እግዚአብሔር*፤ ከባቢሎናውያን ጋር ብትዋጉ አይሳካላችሁም" ይላል' ትላለህ።"

[6]ኤርምያስም የእግዚአብሔር ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ አለ፦ [7]"የአጎትህ የሰሎም ልጅ አናምኤል ወደ አንተ መጥቶ፣ 'የመቤዠት መብት የአንተ ስለሆነ፣ በዓናቶት ያለውን መሬቴን ግዛኝ' ይልሃል።"

[8]*እግዚአብሔርም* እንደ ተናገረኝ፣ የአጎቴ ልጅ አናምኤል ወደ ዘብ ጠባቂዎቹ አደባባይ መጥቶ፣ "የመቤዠቱን ርስት የማድረጉ መብት የአንተ ስለ ሆነ፣ በብንያም አገር በዓናቶት ያለውን መሬቴን ለራስህ እንዲሆን ግዛው" አለኝ። ይህም *የእግዚአብሔር* ቃል እንደ ሆነ ዐወቅሁ፤ [9]ስለዚህ በዓናቶት ያለውን መሬት ከአጎቴ ልጅ ከአናምኤል ገዛሁ፤ ዐሥራ ሰባት ሰቅል[ሠ] ብር መዝኜ ሰጠሁት። [10]በውሉም ሰነድ ላይ ፈረምሁ፤ አሸግሁትም። ብሩንም በምስክሮች ፊት በሚዛን መዘንሁለት። [11]የስምምነቱ ዝርዝር ያለበትን፣ የታሸገውንና ያልታሸገውን የግዢውን የውል ሰነድ ወሰድሁ፤ [12]በአጎቴም ልጅ በአናምኤልና በውሉ ላይ በፈረሙት ምስክሮች ፊት እንዲሁም በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ ተቀምጠው በነበሩ አይሁድ ሁሉ ፊት ለመሕሤያ ልጅ ለኔርያ ልጅ ለባሮክ ሰጠሁት።

[13]በእነርሱ ፊት ለባሮክ እንዲህ የሚል ትእዛዝ ሰጠሁት፤ [14]"የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'የታሸገውንና ያልታሸገውን፣ ሁለቱን የግዢ ውል ሰነዶች ለብዙ ጊዜ ሳይበላሹ እንዲቈዩ ወስደህ በሸክላ ዕቃ ውስጥ አኑራቸው። [15]የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ ሰዎች በዚህ ምድር ቤት፣ የዕርሻ ቦታና የወይን አትክልት ስፍራ እንደ ገና ይገዛሉ።' "

[16]"ለኔርያ ልጅ ለባሮክ የግዢ ውሉን ከሰጠሁ በኋላ፣ ወደ *እግዚአብሔር* እንዲህ ብዬ ጸለይሁ፤

32፥1 2ነገ25፥1፤ ኤር25፥1
32፥2 2ነገ25፥1፤ ነህ3፥25፤መዝ 88፥8
32፥3 ቍ28፤ኤር 21፥4፤26፥8-9፤ 34፥2-3
32፥4 ቍ24፤ኤር 21፥7፤34፥21፤38፥18፤ 23፤39፥5-7፤44፥30፤ 52፥9
32፥5 2ነገ25፥7፤ ኤር21፥4፤39፥7፤ሰቆ 1፥14፤ሕዝ12፥13
32፥7 ዘሌ25፥24-25፤ሩት4፥3-4፤ኢሳ 21፥18፤ማቴ27፥10
32፥8 ቍ25
32፥9 ዘፍ23፥16፤ ኤር37፥12
32፥10 ዘፍ23፥20 ፤ሩት4፥9፤ኢሳ8፥2
32፥12 ቍ16፤ኤር 36፥4፤43፥3፡6፤ 45፥1፤51፥59
32፥14 ኢሳ8፥16
32፥15 ቍ43-44፤ ኢሳ44፥26፤ኤር30፥ 18፤ሕዝ28፥26፤አሞ 9፥14-15
32፥16 ቍ12
32፥17 ዘፍ1፥1፤ዘዳ 9፥29፤2ነገ3፥18፤ 19፥15፤መዝ102፥25 ፤ኤር1፥6፤10፥16፤ 51፥15፤ማቴ19፥26

[ሠ]4 ወይም *ከለዳውያን*፤ በቍ 5:24:25:28:29:እና 43 ይመ።
[ሠ]9 200 ግራም ያህል ነው።

(2፥23ና ማብ ይመ)። *ፈረስ በር*፤ የነህ3፥28 ማብ ይመ። *ለእግዚአብሔር የተቀደሰ*፤ ዘካ14፥20 እና ማብ ይመ። *አትነቀልም፤ አትፈርስምም*፤ የ1፥10 ማብ ይመ።

*32፥1-44*፤ የባቢሎን ሰራዊት ኢየሩሳሌምን መክበብ በጀመረበት ወቅት (ቍ2፡24 ይመ)፣ ኤርምያስ ትንሽ ቢያንገራግርም (ቍ25 ይመ) እግዚአብሔር ዓናቶት ላይ ከአጎቱ መሬት እንዲገዛ ያዘዘውን (ቍ8-9 ይመ) ለመፈጸም ፈቃደኛ ሆነ።

32፥1 *ሴዴቅያስ በነገሠ በዐሥረኛው ዓመት ... በናቡከደነፆር ዐሥራ ስምንተኛ ዘመነ መንግሥት*፤ ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምን ከማጥፋታቸው ከአንድ ዓመት በፊት በ587 ዓ.ቅ.ክ ላይ ማለት ነው (52፥12-13 ይመ)። ከበባው የተጀመረው በ588 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነበር (39፥1፤ 52፥4 ይመ)።

32፥2 *በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ ተዘግቶበት ነበር*፤ ነህ 3፥25 እና ማብ ይመ። ኤርምያስን ያሰረው ንጉሥ ሴዴቅያስ ነበር (37፥21 ይመ)፤ በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ እንደ ታሰረም እስከ ኢየሩሳሌም መውደቅ ድረስ ቈየ (38፥13:28፤ 39፥14 ይመ)።

*32፥3-5*፤ 21፥3-7፤ 34፥2-5፤ 37፥17 ይመ። ትንቢቱ በ52፥7-14 ተፈጽሞአል።

32፥5 *በፍርዴ እስከምጐበኘውም ድረስ*፤ ሴዴቅያስ በባቢሎናውያን ከተያዘ በኋላ በምርኮ ወደ ባቢሎን ተወስዶአል፤ በመጨረሻም እዚያው እንዳለ ሞቶአል (52፥11 ይመ)። *አይሳካላችሁም*፤ የ29፥4 ማብ ይመ።

32፥7 *ዓናቶት*፤ ኤርምያስ ተወልዶ ያደገባት ከተማ ናት (የ1፥1 ማብ ይመ)። *የመቤዠት መብት የአንተ ስለ ሆነ*፤ በጥንቱ የመዋጀት ሕግ ወይም ደንብ መሠረት ማለት ነው (ዘሌ 25፥23-25 ይመ፤ በተጨማሪም የሩት2፥20፤ 4፥3 ማብ ይመ)።

32፥8 *ወደ ዘብ ጠባቂዎቹ አደባባይ መጥቶ*፤ ኤርምያስ በእስር ላይ ቢሆንም እንኳ ጠያቂ አልተከለከለበትም ነበር። *በብንያም አገር*፤ ከዚህ ቀደም ብሎ፣ ኤርምያስ በብንያም አገር ከነበረው ንብረት ላይ ድርሻውን ለመቀበል ሄዶ ነበር (37፥12)፤ ነገር ግን አገሩን ከድቶአል ተብሎ በሐሰት በመከሰስ ታስሮ ነበር (37፥13-16) ይመ)።

32፥9 *ስለዚህ ... ገዛሁ*፤ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ተቀብሎ ማለት ነው (ቍ7 ይመ)። *መዝኜ*፤ በዚህ ጊዜ በጥሬ ገንዘብ መገበያየት አይታወቅም ነበር። *ዐሥራ ሰባት ሰቅል ብር*፤ ሁለት መቶ ግራም ያህል ይሆናል። የተገዛው መሬት መጠን ባይታወቅም፣ ዋጋው እስከዚህ የሚበዛበት አልነበረም (ከዘፍ23፥15 ጋር ያገናዝቡ፤ የዚያኑ ማብ ይመ)።

32፥10 *አሸግሁትም*፤ እንዲህ ያደረገው በፊርማው ለማረጋገጥ ሳይሆን (ለምሳሌ፦ በአስ3፥12 እንዳለው፣ የዘፍ38፥18 ማብ ይመ)፣ ዋስትና እንዲኖረውና የተጻፈው ቃል እንዳይፋለስ ነው (ኢሳ8፥16፤ 29፥11፤ ዳን12፥4:9፤ ራእ15፥1-5 ይመ)።

32፥11 *ያልታሸገውን የግዢውን የውል ሰነድ*፤ ያልታሸገው ሙሉ ቅጅ እንዲሁ ቢጠፋ ወይም ሆን ተብሎ እንዲጠፋ ቢደረግ፣ ቢበላሽ ወይም ቢለወጥ፣ የታሸገውን ትክክለኛ ቅጅ ለማመሳከርና ለማረጋገጥ አስተማማኝ ዋስትና አለው።

32፥12 *ባሮክ*፤ "የተባረከ (በጌታ)" ማለት ነው። ለኤርምያስ ታማኝ ጸሓፊውና ወዳጁ ነበር።

32፥14 *ለብዙ ጊዜ ሳይበላሹ እንዲቈዩ ... በሸክላ ዕቃ ውስጥ አኑራቸው*፤ በግብፅ ኤሌፋንታይን በተባለ ቦታ፣ እንዲሁም ከሙት ባሕር በስተ ምዕራብ በሚገኘው በቁምራን ከሁለት ሺህ ዓመት በላይ ዕድሜ ያላቸው ጽሑፎች ሳይበላሹና ምንም ሳይሆኑ እንዲሁ እንዳሉ ተገኝተዋል።

*32፥15*፤ ኤርምያስ የዕርሻ መሬት (እንዲሁም ለወራሾቹ) ለመግዛት ውል የፈረመው ከምርኮ በኋላ ሰላምና ዕረፍት በምድሪቱ ላይ ሲሰፍን የገዛውን መሬት መልሶ ለመያዝ እንዲያስችለው ነው።

[17]“አቤት፣ ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ ሰማያትንና ምድርን በታላቅ ኀይልህና በተዘረጋች ክንድህ ፈጥረሃል፤ የሚሳንህም አንዳች ነገር የለም። [18]ፍቅርና ቸርነትን ለእልፍ አእላፍ ታሳያለህ፤ ይሁን እንጂ የአባቶችን በደል ከእነርሱ በኋላ በሚነሡ ልጆቻቸው ጉያ ትመልሳለህ፤ ስምህ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* የሆነ፣ ታላቅና ኀያል ስሜሳክ ሆይ፤ [19]ዕቅድህ ታላቅ፣ በሥራም ብርቱ ነህ፤ ዐይኖችህ የሰው ልጆችን መንገዶች ሁሉ ያያሉ፤ ለእያንዳንዱም እንደ መንገዱና እንደ ሥራው ትከፍለዋለህ። [20]በግብፅ ታምራትንና ድንቆችን አደረግህ፤ እስከ ዛሬም ድረስ በእስራኤልና በሰው ልጆች ሁሉ መካከል እንደዚያው እያደረግህ ዛሬም ስምህ ገናና ነው። [21]በታምራትና በድንቅ፣ በብርቱ እጅና በተዘረጋች ክንድ፣ እጅግ በሚያስፈራም ግርማ ሕዝብህን እስራኤልን ከግብፅ አወጣህ። [22]ለአባቶቻችን ልትሰጣቸው የማልህላቸውን፣ ማርና ወተት የምታፈሰውን ይህችን ምድር ሰጠሃቸው፤ [23]ወደዚያም ገብተው ወረሷት፤ ነገር ግን አልታዘዙህም፤ ሕግህንም አልጠበቁም፤ እንዲያደርጉት ያዘዝሃቸውን ከቶ አላደረጉም፤ ስለዚህ ይህን ሁሉ ጥፋት በላያቸው አመጣህ።

[24]“እነሆ፤ ከተማዪቱን ለመያዝ የዐፈር ድልድል በዙሪያዋ ተሠርቶአል፤ ከሰይፍ፣ ከራብና ከቸነፈር የተነሣ ከተማዪቱን ለሚወጓት ለባቢሎናውያን ዐልፋ ልትሰጥ ነው፤ እንደምታየውም የተናገርኸው እየተፈጸመ ነው። [25]አንተ ግን ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ከተማዪቱ ለባቢሎናውያን ዐልፋ እየተሰጠች፣ ‘መሬቱን በብር ግዛ፤ ግዢውንም በምስክሮች ፊት ፈጽም’ ትለኛለህ።”

[26]ከዚያም በኋላ የ*እግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [27]“እነሆ፤ እኔ የሰው ልጆች ሁሉ ስሜሳክ *እግዚአብሔር* ነኝ፤ በውኑ የሚያቅተኝ ነገር አለን? [28]ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ እነሆ፤ ይህቺን ከተማ ለባቢሎናውያንና ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደናፆር አሳልፌ እሰጣታለሁ፤ እርሱም ይይዛታል። [29]ከተማዪቱን የሚወጓት ባቢሎናውያን ወደ ውስጥ ይገባሉ፤ በእሳትም ያቃጥሏታል፤ ያስቈጡኝ ዘንድ ሕዝቡ በየሰገነቱ ላይ ለበኣል ያጠኑባቸውንና ለሌሎችም አማልክት የመጠጥ ቍርባን ያቀረቡባቸውን ቤቶች ጭምር ያነዳሉ።

[30]“የእስራኤል ሕዝብና የይሁዳ ሕዝብ ከታናሽነታቸው ጀምሮ ከክፉ ነገር በቀር በፊቴ አንዳች በጎ ነገር አልሠሩም፤ በእርግጥም የእስራኤል ሕዝብ በእጃቸው ሥራ አስቈጡኝ፤ ይላል *እግዚአብሔር*። [31]ይህች ከተማ፣ ከተመሠረተችበት ጊዜ አንሥቶ እስከ ዛሬ ድረስ ከፊቴ እንዳስወግዳት ቍጣዬንና መዓቴን አነሣሥታለች፤ [32]የእስራኤልና የይሁዳ ሕዝብ፦ እነርሱ፣ ነገሥታታቸው፣ ባለሥልጣኖቻቸው፣ ካህናታቸው፣ ነቢያታቸው፣ የይሁዳ ሰዎችና የኢየሩሳሌም ነዋሪዎች ባደረጉት ክፋት ሁሉ አስቈጡኝ። [33]ፊታቸውን ሳይሆን ጀርባቸውን ሰጡኝ፤ ደጋግሜ ባስተምራቸውም አይሰሙም፤ ተግሣጽም አይቀበሉም። [34]ስሜ በተጠራበት ቤት አስጸያፊ ጣዖታቸውን አቆሙ፤ አረከሱትም። [35]ወንዶችና ሴቶች[a] ልጆቻቸውን ለሞሌክ ይሠው ዘንድ በሄኖም ሸለቆ ለበኣል መስገጃ ኰረብቶችን ሠሩ፤ ነገር ግን

[a]35 ወይም *ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን በእሳት ያሳልፉ ዘንድ*

32፥18 ዘፀ20፥5፤ዘዳ5፥10፤መዝ79፥12፤10 9፥14፤ኤር10፥6፡16
32፥19 ኢዮ12፥13፤14፥16፤34፥11፤ምሳ 5፥21፤ኤር16፥17፤ ዳን2፥20፤ማቴ16፥27
32፥20 ዘፀ3፥20፤ 9፥16፤ኢዮ9፥10፤ኢሳ 55፥13፤ኤር13፥11
32፥21 ዘፀ6፥6፤ዘዳ 5፥15፤26፥8፤ኤር 6፥12፤ዳን9፥15
32፥22 ዘፀ3፥8፤ሕዝ 20፥6
32፥23 ዘፀ16፥28፤ ዘዳ28፥64፤31፥29፤ ኢሱ1፥7፤1ነገ9፥6፤ መዝ44፥2፤78፥54-55 ፤ኤር11፥8፤ዳን9፥14
32፥24 ዘዳ4፥25-26 ፤28፥2፤ኢሱ23፥15-16፤ 2ሳሙ20፥15፤ ኤር6፥6፤14፥12
32፥25 ቊ8፤ኢሳ 8፥2
32፥27 ዘፍ18፥14፤ ዘኊ16፥22፤2ነገ3፥18
32፥28 ቊ3፤2ዜና 36፥17፤ ኤር21፥10
32፥29 2ዜና36፥19 ፤ኤር7፥9፤19፥13፤ 44፥18
32፥30 መዝ25፥7፤ ኤር8፥19፤22፥21፤ 25፥7
32፥31 1ነገ11፥7-8 ፤2ነገ21፥4-5፤23፥27፤ ማቴ23፥37
32፥32 1ነገ14፥9፤ ኤር2፥26፤ 44፥9፤ ዳን9፥8
32፥33 ዘዳ4፥5፤ 1ነገ14፥9፤መዝ14፥3 ፤ኢሳ28፥9፤ኤር2፥27፤ 7፥13፡28፤ሕዝ8፥16፤ ዘካ7፥11

*32፥17፤* 27፥5 ይመ። *በታላቅ ኀይልና በተዘረጋች ክንድህ፤* ቊ21 ይመ፤ በተጨማሪም የ21፥5 ማብ ይመ።*የሚሳንህም አንዳች ነገር የለም፤* የዘፍ18፥14 ማብ ይመ። እግዚአብሔር ለኤርምያስ የሰጠው መልስም ይህንኑ ያንጸባርቃል (ቊ27 ይመ)።

32፥18 *ፍቅርና ቸርነትን ለእልፍ አእላፍ ... ይሁን እንጂ የአባቶችን በደል በ ... በልጆቻቸው ... ትመልሳለህ፤* ዘፀ20፥5-6፤ 34፥7 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፀ20፥6 ማብ ይመ። *በ...ጉያ ትመልሳለህ፤* ብድራት መመለስን የሚያመለክት ምሳሌያዊ አባባል ነው (መዝ 79፥12፤ ኢሳ 65፥6-7 ይመ፤ ከሉቃ 6፥38 ጋር ያነጻጽሩ)። *ታላቅና ኀያል አምላክ፤* ዘፀ10፥17 ይመ። *ስምህ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤* 31፥15፤ ኢሳ54፥5፤ አሞ4፥13 ይመ።

32፥19 *ዕቅድህ ታላቅ፣ በሥራም ብርቱ፤* መዝ66፥5፤ ኢሳ 9፥6፤ 28፥29 ይመ። *ለእያንዳንዱም እንደ ... ሥራው ትከፍለዋለህ፤* ከ17፥10 ቃል በቃል የተወሰደ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ፤ በተጨማሪም 1ቆሮ3፥18፤ ኤፌ6፥8 ይመ)።

32፥20 *ታምራትንና ድንቆችን፤* ቊ21 ይመ፤ ዘፀ7፥3 በተጨማሪ ይመ፤ እንዲሁም የዘፀ3፥12፤ 4፥8 ማብ ይመ። *እስከ ዛሬም ድረስ፤* 11፥7 ይመ።

*32፥21፤* ከዘዳ26፥8 ላይ ከሞላ ጎደል ቃል በቃል የተወሰደ (ዘዳ4፥34 ይመ)። *በብርቱ እጅና በተዘረጋች ክንድ፤* ቊ17 እና የ21፥5 ማብ ይመ። *እጅግ በሚያስፈራም ግርማ፤* ዘፀ 15፥14-16 ይመ።

32፥22 *ማርና ወተት የምታፈሰውን ... ምድር፤* 11፥5 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፀ3፥8 ማብ ይመ።

32፥24 *የዐፈር ድልድል፤* 6፥6፤ 33፥4 ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ37፥33 ይመ። *ከሰይፍ፣ ከራብና ከቸነፈር፤* የ14፥12 ማብ ይመ።

*32፥25፤* ኤርምያስ ነገሩ የአላዋቂ ተግባር መስሎ ስለ ታየው ገንዘቡን የትም እንደ ጣለ ተሰምቶት፣ ጥርጣሬውን ይገልጻል፤ ይሁን እንጂ ፍጹም ታዛዥነቱ አልተጓደለም (ቊ8-9 ይመ)።

32፥27 *የሰው ልጆች ሁሉ አምላክ እግዚአብሔር፤* ዘኊ16፥22፤ 27፥16 ላይ ያለውን ያንጸባርቃል፤ ይህም እግዚአብሔር የፍጥረተ ዓለም ሁሉ ጌታ መሆኑን በአጽንዖት ያሳያል። *በውኑ የሚያቅተኝ ነገር አለን?* በኤርምያስ ጸሎት ውስጥ በዝርዝር ለቀረበው ሐሳብ የተሰጠ መልስ ነው (ቊ17 እና የዘፍ 18፥14 ማብ ይመ)፤ ይህ በአጽንዖት የሚያሳየውም የእግዚአብሔርን ሁሉን ቻይነት ነው። እግዚአብሔር የገባውን ቃል ለመፈጸም ምን ጊዜም ታማኝ ስለ ሆነ፤ ልንታዘዘው ይገባል።

32፥29 *በእሳትም ያቃጥሏታል፤* 21፥10፤ 34፥2፤ 37፥8 ይመ። *ያስቈጡኝ ዘንድ፤* 7፥18፤ ዘዳ31፥29 ይመ። *ለበኣል ያጠኑባቸውንና፤* 1፥16 እና ማብ ይመ። *በየሰገነቱ ላይ፤* የ19፥13 ማብ ይመ። *ለሌሎችም አማልክት የመጠጥ ቍርባን ያቀረቡባቸውን፤* 7፥18 እና ማብ፤ 19፥13 ይመ።

*32፥30፤* በዘዳ31፥29 ላይ ያለው ሐሳብ በዚህ ውስጥ ይንጸባረቃል። *ከታናሽነታቸው፤* የ31፥19 ማብ ይመ። *በእጃቸው ሥራ፤* ጣዖታትን ያመለክታል።

32፥31 *ከፊቴ እንዳስወግዳት፤* 52፥3፤ 2ነገ24፥3 ይመ።

32፥32 *ነገሥታታቸው፣ ባለሥልጣናቶቻቸው፣ ካህናታቸው፣ ነቢያታቸው፤* 1፥18 እና ማብ ይመ።

32፥33 *ደጋግሜ፤* የ7፥13 ማብ ይመ። *ተግሣጽም አልተቀበሉም፤* 2፥30፤ 5፥3፤ 7፥28፤ 17፥23 ይመ።

*32፥34-35፤* ከ7፥30-31 ላይ የተወሰደ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)።

32፥35 *ሞሌክ፤* የአሞናውያን ጣዖት ነው (49፥1፡3 ይመ፤ በተጨማሪም የዘሌ18፥21 ማብ ይመ)።

ይሁዳን ኀጢአት ለማሠራት እንደዚህ ያለ ውን አስጸያፊ ተግባር እንዲፈጽሙ እኔ አላዘዝሁም፤ ከቶም አላሰብሁም::

[36]“ ‘በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር ለባቢሎን ንጉሥ ዐልፋ ትሰጣለች’ ስላልሃት ስለዚህች ከተማ፣ የእስራኤል አምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ [37]“በጽኑ ቍጣዬና በታላቅ መቅሠፍቴ እነርሱን ካሳደድሁበት ምድር ሁሉ በእውነት እሰበስባቸዋለሁ፤ ወደዚህም ስፍራ እመልሳቸዋለሁ፤ በሰላምም እንዲ ቀመጡ አደርጋቸዋለሁ:: [38]እነርሱ ሕዝብ ይሆኑኛል፤ እኔም አምላክ እሆናቸዋለሁ:: [39]ለእነርሱና ከእነርሱም በኋላ ለልጆቻቸው መልካም እንዲሆንላቸው ዘወትር ይፈሩኝ ዘንድ፣ አንድ ልብ አንድም ሐሳብ እሰጣቸ ዋለሁ:: [40]መልካምን ነገር ለእነርሱ ከማድ ረግ እንዳልቈጠብና ከእኔም ፈቀቅ እንዳ ይሉ መፈራቴን በውስጣቸው ላኖር ከእነ ርሱ ጋር የዘላለም ቃል ኪዳን እገባለሁ:: [41]ለእነርሱ መልካም በማድረግ ደስ ይለኛል፤ በፍጹም ልቤና በፍጹም ነፍሴ በእውነት በዚህች ምድር እተክላቸዋለሁ::’ ”

[42]“*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ‘በዚህ ሕዝብ ላይ ይህን ሁሉ ታላቅ ጥፋት እንዳመጣሁ እንደዚሁ ቃል የገባሁላቸውን መልካም ነገር ሁሉ እሰጣቸዋለሁ:: [43]እናን ተም፣ “ለባቢሎናውያን ዐልፋ ስለ ተሰጠች፣ ሰውና እንስሳ የማይኖሩባት ባድማ ናት” ባላችኋት በዚህች ምድር እንደ ገና መሬት ይገዛል:: [44]ምርኮአቸውን ስለምመልስላቸው[a] በብንያም አገር፣ በኢየሩሳሌም ዙሪያ ባሉ መንደሮች፣ በይሁዳ ከተሞችና በተራራ ማው አገር ከተሞች፣ በምዕራብ ተራሮች ግርጌና በኔጌብ ባሉ ከተሞች መሬት በጥሬ ብር ይገዛል፤ ውሉም ተፈርሞ፣ በምስክሮች ፊት ይታሸጋል፤ ይላል *እግዚአብሔር*::’ ”

32፥34 2ነገ21፥4፤ ኤር7፥10፤7፥30፤ 34፥15፤ሕዝ 8፥3-16
32፥35 ዘሌ18፥21፤ 1ነገ14፥24፤ኤር19፥5 ፤25፥7
32፥36 ቍ24
32፥37 ዘሌ25፥18፤ ኢሳ11፥12፤21፥5፤ ሕዝ34፥28፤39፥26
32፥38 ኤር24፥7፤ 2ቆሮ6፥16
32፥39 ዘዳ6፥24፤ 10፥16፤2ዜና30፥12፤ መዝ86፥11፤ዮሐ 17፥21፤ሐሥ4፥32
32፥40 ዘፍ9፥16፤ ዘዳ4፥10፤ኢሳ42፥6፤ ኤር24፥7
32፥41 ዘዳ28፥3-12 ፡63፤ኢሳ62፥4፤ኤር 24፥6፤31፥28፤ሚክ 7፥18
32፥42 ኤር29፥10፤ ሰቆ3፥38
32፥43 ቍ15፤ኤር 33፥12
32፥44 ቍ10፤ሩት 4፥9፤ዕዝ9፥9፤መዝ 14፥7፤ኢሳ8፥2፤ኤር 17፥26
33፥1 መዝ88፥8፤ ኤር13፥3፤37፥21፤ 38፥28
33፥2 ዘፀ3፥15፤መዝ 136፥6፤ኤር10፥16
33፥3 ኢዮ28፥11፤ ኢሳ55፥6
33፥4 2ነገ25፥1፤ ኤር32፥24፤ሕዝ4፥2፤ 26፥8፤ዕን1፥10
33፥5 ዘዳ31፥17፤ ኢሳ8፥17፤ኤር21፥4-7

## የመመለስ ተስፋ

**33** ኤርምያስ በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ በግዞት ሳለ *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ዳግመኛ ወደ እርሱ መጣ:- [2]“ምድርን የፈጠራት፣ ያበጀትና የመሠረ ታት *እግዚአብሔር*፣ ስሙ *እግዚአብሔር* የ ሆነ፣ እርሱ እንዲህ ይላል፤ [3]‘ወደ እኔ ጩኽ፤ እኔም እመልስልሃለሁ፤ አንተም የማ ታውቀውን ታላቅና የማይመረመር ነገር እገልጥልሃለሁ፤’ [4]የእስራኤል አምላክ *እግዚ አብሔር* ከባቢሎናውያን[b] ጋር ባለው ውጊያ፣ ዐፈር በመደልደልና በሰይፍ የሚደረገውን ጥቃት ለመከላከል ስለ ፈረሱት ስለዚህች ከተማ ቤቶችና ስለ ይሁዳ ነገሥታት ቤተ መንግሥት እንዲህ ይላል፤ [5]‘እነዚህ በቍጣዬና በመዓቴ በምገድላቸው ሰዎች ሬሳ ይሞላሉ፤ ስለ ክፋቷ ሁሉ ከዚህች ከተማ ፊቴን እሰውራለሁ::

[6]“ ‘ይሁን እንጂ፣ ፈውስንና ጤንነትን እንደ ገና እሰጣታለሁ፤ ሕዝቤንም እፈውሳ ለሁ፤ በብዙ ሰላምና በርጋታ እንዲኖሩ አደርጋለሁ:: [7]የይሁዳን ምርኮና የእስራ ኤልን ምርኮ እመልሳለሁ፤[c] ቀድሞ እንደ

[a]44 ወይም *ከምርኮ ስለምመልሳቸው*
[b]4 ወይም *ከለዳውያን*
[c]7 ወይም *ይሁዳንና እስራኤልን ከምርኮ እመልሳለሁ*

32፥36 *በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር፤* የ14፥12 ማብ ይመ::

*32፥37፤* ዘዳ30፥1-5 ይመ፤ *በጽኑ ቍጣዬና በታላቅ መቅ ሠፍቴ፤* የ21፥5 ማብ ይመ:: *እመልሳቸዋለሁ ... እንዲቀመጡ አደርጋቸዋለሁ፤* ሕዝ36፥11፡33፤ ሆሴ11፥11 ይመ:: በዕብራይስጥ የመጀመሪያው ሐረግ ድምፀት የሁለተኛውን ሐረግ ድምፀት ይመ ስላል::

*32፥38፤* 31፥33 ይመ፤ በተጨማሪም የ7፥23 ማብ ይመ::

32፥39 *አንድ ልብ፤* 24፥7፤ 31፥32 እና ማብ፤ ሕዝ11፥19 ይመ፤ *ከእነርሱም በኋላ ለልጆቻቸው፤* ዘዳ4፥9-10 ይመ::

32፥40 *የዘላለም ቃል ኪዳን፤* ኢሳ55፥3 እና ማብ፤ ሕዝ 16፥60፤ 37፥26 ይመ:: እንደ ቀድሞው ኪዳን (31፥32፤ ኢሳ 24፥5 ይመ) አዲሱ ኪዳን ፈጽሞ ሊጣስ አይገባውም:: *መፈራቴን በውስጣቸው ላኖር፤* ዘዳ6፥24 ይመ፤ በተጨማሪም የዘፍ20፥11 ማብ ይመ:: *ከእኔም ፈቀቅ እንዳይሉ፤* 26፥3፤ ኢሳ53፥6 ይመ::

32፥41 *ለእነርሱ መልካም በማድረግ ደስ ይለኛል፤* ዘዳ30፥9፤ ኢሳ62፥5፤ 65፥19 ይመ::

32፥43-44 *መሬት ይገዛል፤* ኤርምያስ የገዛው መሬት (ቍ9 ይመ)፣ ከባቢሎን ምርኮ መልስ በኋላ የኢኮኖሚ ሁኔታዎች ሲረ ጋጉ (የቍ15 ማብ ይመ)፣ በይሁዳ የሚገዙ ብዙ የእርሻ መሬ ቶች ምሳሌ ነው::

32፥43 *ባላችኋት (እናንተ)፤* የቍ36 ማብ ይመ:: *ሰውና እንስሳ የማይኖሩባት ባድማ፤* 4፥23-26 እና ማብ ይመ::

32፥44 *በብንያም አገር፤* 1፥1 ይመ:: እዚህ ላይ ብንያም በቅድሚያ የተጠቀሰው፣ ኤርምያስ የተወለደባት ስፍራ የምትገኝ በት አገር ስለ ሆነ ነው (ቍ7-ም እና ማብ ይመ):: *በተራራማው አገር ... በምዕራብ ተራሮች ግርጌና፤* የዘዳ1፥7 ማብ ይመ:: *በኔጌብ፤* የዘፍ12፥9 ማብ ይመ:: *ምርኮአቸውን ስለምመልስ ላቸው፤* የ29፥14 ማብ ይመ::

*33፥1-26፤* የኤርምያስን “የመጽናናት መጽሐፍ” (የ30፥ 1-33፥26 ማብ ይመ) የሚደመድመው ይህ ክፍል በሁለት ይከፈ ላል፤ 1) ቍ1-13 ቀጣይ ሐሳብ ያለው የምዕራፉ አካል ነው፤ 2) ከዚህ ቀደም ሲል ባለው ክፍል በስፋት የተጻፉትንና በሌላ ቦታ የሚገኙትን የኤርምያስን መልእክቶች አጠቃሎ የሚያቀርብ ሲሆን፣ በሰብዓ ሊቃናት (በግሪኩ የብሉይ ኪዳን) ትርጒም ግን አይገኝም::

33፥1 *በግዞት ሳለ፤* በ587ዓ.ቅ.ክ ላይ ማለት ነው (የ32፥1 ማብ ይመ):: *በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ፤* 32፥2 እና ማብ ይመ:: *ዳግመኛ፤* ም32 «መጀመሪያ» የሚለውን ቃል ይይዛል::

*33፥2፤* 10፥12፤ 32፥17፤51፥15 እንዲሁም 31፥35 እና ማብ ይመ::

33፥3 *ጩኽ ... እመልስልሃለሁ፤* ሰዎች የሚያቀርቡት ጸሎት መልስ እንዲሰጥ እግዚአብሔርን የሚጋብዝ ነው፤ የእግዚ አብሔር መልስ እንደሚኖርም ማረጋገጫ ሊሆን ይችላል (መዝ 3፥4፤ 4፥3፤ 18፥6፤ 27፥7፤28፥1-2፤ 30፥8፤ 55፥17፤ ማቴ7፥7 ይመ፤ ከ11፥14 ጋር ያነጻጽሩ):: *ታላቅና የማይመረመር፤* በዕብራ ይስጥ ለዚህ ሐረግ የተሰጠው ትርጒም ታላላቆቹን የከነዓን ከተ ሞች ያመለክታል፤ እርሱም፣ “ሰማይ ጠቀስ ቅጥር ያላቸው ታላ ላቅ ከተሞች” ይላቸዋል (ዘዳ1፥28፤ ዘኍ13፥28፤ ዘዳ9፥1፤ ኢያ 14፥12 ይመ):: *የማታውቀውን ... የማይመረመር ነገር፤* በዕብራ ይስጡ አንዷ ሆሄ ስትለወጥ ይህ ሐረግ የሚሰጠው ትርጒም፣ “የተሰወሩትን ያላወቅሃቸውንም” (ኢሳ48፥6) የሚለውን ያስተጋ ባል:: እግዚአብሔር በመጀመሪያ በሕዝቡ ላይ ይፈርዳል (ቍ4-5)፤ ከዚያም በሚያስደንቅ ሁኔታ ይታደጋቸዋል (6-26)::

*33፥4፤* በኢየሩሳሌም ያሉ ሕንጻዎችና የነገሥታት መኖሪ ያዎች ተደመሰሱ፤ ድንጋዮቻቸውም የአጥር መጠገኛ ሆነዋል (ኢሳ 22፥10 እና ማብ ይመ):: *ዐፈር በመደልደል፤* ጠላት በኢየሩሳ ሌም ቅጥር ላይ እንዲወጣ የሚረዳ ነው (6፥6 ይመ):: *ከባቢ ሎናውያን ጋር ባለው ውጊያ፤* 32፥5 ይመ::

33፥5 *ሬሳ፤* ኢየሩሳሌምን የሚጠብቋትን ሰዎች/ሬሳ ነው::

33፥6 *ፈውስንና ጤንነትን፤* 30፥17 ይመ፤ ከ8፥22 ጋር ያነጻጽሩ::

33፥7 ... *ምርኮ እመልሳለሁ፤* ቍ11፡26 እንዲሁም የ29፥14 ማብ ይመ:: *የይሁዳን ... እና ... የእስራኤልን፤* የ3፥18

ነበሩት ሁኔታ አድርጌ አበጃቸዋለሁ፤ [8]እኔን ከበደሉበት ኀጢአት ሁሉ አነጻቸዋለሁ፤ በእኔ ላይ ያመፁበትንም ኀጢአታቸውን ሁሉ ይቅር እላለሁ። [9]ይህች ከተማ፣ ለእርሷ ያደረግሁትን በጎ ነገር ሁሉ በሚሰሙት የምድር ሕዝቦች ሁሉ ፊት ለዝና፣ ለደስታ፣ ለምስጋናና ለክብር ትሆናለች፤ ከምሰጣትም የተትረፈረፈ ብልጽግናና ሰላም የተነሣ ይፈራሉ፤ ይንቀጠቀጣሉም።'

[10]"*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ይህችን ስፍራ፣ 'ሰውና እንስሳት የማይኖሩባት ባድማ ናት' ትላላችሁ፤ ነገር ግን ሰውም ሆነ እንስሳ ባልነበሩባቸውና ባድማ በሆኑት በይሁዳ ከተሞችና በኢየሩሳሌም መንገዶች፣ እንደ ገና ድምፅ ይሰማል፤ [11]የሐሤትና የደስታ ድምፅ፣ የሙሽራውና የሙሽራዪቱ ድምፅ፣ እንዲሁም፦

"*እግዚአብሔር* ቸር ነውና፤
ምሕረቱም ለዘላለም ነውና፤
የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔርን*
አመስግኑ፤"

የሚል የምስጋናን መሥዋዕት ይዘው ወደ *እግዚአብሔር* ቤት የሚመጡ ሰዎች ድምፅ ይሰማል፤ የምድሪቱን ምርኮ ቀድሞ እንደ ነበረ እመልሳለሁና፤ ይላል *እግዚአብሔር*።

[12]"የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ሰውም ሆነ እንስሳት በማይኖሩበት በዚህ ባዶ ስፍራ፣ በከተማዎቹም ሁሉ እረኞች መንጎቻቸውን የሚያሳርፉበት እንደ ገና ያገኛሉ። [13]በተራራማው አገር፣ በምዕራብ ተራሮች ግርጌና በኔጌብ ባሉ ከተሞች በብንያም አገር፣ በይሁዳ ከተሞች እንዲሁም በኢየሩሳሌም ዙሪያ ባሉ መንደሮች መንጎች እንደ ገና በሚቈጥራቸው ሰው እጅ ሥር ያልፋሉ' ይላል *እግዚአብሔር*።

[14]" 'ለእስራኤል ቤትና ለይሁዳ ቤት የገባሁትን የተስፋ ቃል የምፈጽምበት ጊዜ ይመጣል' ይላል *እግዚአብሔር*።

[15]" 'በዚያ ዘመንና በዚያ ጊዜ፣
ከዳዊት ቤት ጽድቅ ቅርንጫፍ
አበቅላለሁ፤
በምድሪቱም ፍትሕንና ጽድቅን
ያደርጋል።
[16]በዚያ ዘመን ይሁዳ ይድናል፤
ኢየሩሳሌም በሰላም ትኖራለች፤
የምትጠራበትም ስም፣
"*እግዚአብሔር ጽድቃችን*" የሚል
ይሆናል።'

[17]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ 'ከዳዊት ዘር በእስራኤል ቤት ዙፋን ላይ የሚቀመጥ ሰው ፈጽሞ አይታጣም፤ [18]ሌዋውያን ከሆኑት ካህናትም የሚቃጠል መሥዋዕት ለማቅረብ፣ የእህል ቍርባን ለማቃጠልና ሌላውንም መሥዋዕት ለመሠዋት ሁል ጊዜ በፊቴ የሚቆም ሰው አይታጣም።' "

[19]የ*እግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [20]"*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ለቀንና ለሌሊት የወሰንሁትን ሥርዐት በማፍረስ ቀንና ሌሊት በተወሰነላቸው ጊዜ እንዳይፈራረቁ ኪዳኔን ማፍረስ ብትችሉ፣ [21]በዚያ ጊዜ ከአገልጋዬ ከዳዊት ጋር የገባሁትን ኪዳን፣ እንዲሁም በፊቴ በክህነት ከሚያገለግሉት ሌዋውያን ጋር የገባሁትን ኪዳን ማፍረስ ይቻላል፤ ዳዊትም ከእንግዲህ በዙፋኑ ላይ የሚነግሥ ዘር አይኖረውም። [22]የአገልጋዬን የዳዊትን ዘር እንዲሁም በፊቴ የሚቆሙትን ሌዋውያን እንደማይቈጠሩ እንደ ሰማይ ከዋክብትና

33፥6 ዘዳ32፥39፤ ኢሳ9፥6፤30፥26
33፥7 ኢሳ1፥26፤ ኤር24፥6፤30፥3፤ 32፥44፤ሕዝ39፥25፤ አሞ 9፥14
33፥8 ዘሌ16፥30፤ 2ሳሙ24፥14፤ኤር 31፥34፤ዕብ 9፥13-14
33፥9 ኢሳ55፥13፤ 60፥18፤64፥2፤ኤር 3፥17
33፥10 ዘሌ26፥32፤ ኤር9፥11፤32፥43
33፥11 ዘሌ7፥12፤ 1ዜና16፥34፤2ዜና5፥13፤7፥3፤መዝ25፥8፤5 1፥8፤100፥4-5፤136፥1 ፤ኢሳ1፥26፤24፥8፤51፥3፤ናሆ1፥7፤14፥7
33፥12 ቍ10፤ኢሳ 65፥10፤ኤር32፥43፤ ሕዝ34፥11-15
33፥13 ዘሌ27፥32፤ ኤር17፥26፤31፥5፤ አብ1፥20
33፥14 ዘዳ28፥1-14 ፤ኢሱ23፥15፤ኤር 29፥10
33፥15 2ሳሙ7፥12 ፤መዝ72፥2፤ኢሳ4፥2
33፥16 ኢሳ45፥17፤ 59፥14፤ኤር3፥17፤ 17፥25፤32፥37፤ሕዝ 48፥35፤ሶፎ3፥13፤ዘካ 8፥3፡16፤1ቆሮ1፥30
33፥17 2ሳሙ7፥13 ፤2ዜና7፥18፤መዝ 89፥29-37፤ ሉቃ 1፥33
33፥18 ዘኍ25፥11 -13፤ዘዳ18፥1፤ዕን13 ፥15፤ዕብ7፥17-22
33፥20 ዘፍ1፥14፤ መዝ89፥36
33፥21 ዘዳ18፥1፤ 2ሳሙ7፥13፤2ዜና 7፥18፤መዝ 9፥34
33፥22 ዘፍ12፥2፤ ኤር30፥19፤ሆሴ1፥10

ማብ ይመ።

33፥8 *ኀጢአታቸውን ሁሉ ይቅር እላለሁ፤* ይህ የአዲስ ኪዳን ሥርዐት መሠረት ነው (31፥34 እና ማብ፤ 50፥20፤ ሕዝ 36፥25-26 ይመ)።

33፥9 *የተትረፈረፈ ብልጽግናና ... ይንቀጠቀጣሉም፤* ሆሴ3፥5 ይመ።

*33፥10፤* 32፥43 እና ማብ ይመ።

33፥11 *የሐሤትና የደስታ ... የሙሽራውና የሙሽራዪቱ፤* በ7፥34፤ 16፥9፤ 25፥10 ላይ የዚህን ተቃራኒ ይመ። *የምስጋናን መሥዋዕት ይዘው ... የሚመጡ፤* የ17፥26 ማብ ይመ። *ምርኮ ... እመልሳለሁና፤* የ29፥14 ማብ ይመ።

33፥13 *በተራራማው አገር ... በይሁዳ ከተሞች፤* 17፥26 እና ማብ፤ 32፥44 ይመ። *መንጎች ... በሚቈጥራቸው ሰው እጅ ሥር ያልፋሉ፤* ሕዝ20፥37 ይመ።

*33፥15-16፤* በ23፥5-6 ላይ ያለው (ማብ ይመ) እዚህ ተደግሞአል።

33፥16 *የምትጠራበትንም ስም፤* ኢየሩሳሌም ከመሲሑ ጋር ካላት የቀረበ ግንኙነት የተነሣ በ23፥6 ላይ ለእርሱ በተሰጠው ስም ተጠርታለች (በመሳ6፥24፤ በሕዝ 48፥35 ላይ ሌሎች ምሳሌዎች ይመ)።

*33፥17-26፤* ምድሪቷን ባድማ ባደረጋት ፍርድ ፊት እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የገባው ቃል ኪዳን (ከእስራኤል፣ ከዳዊትና ከፊንሐስ ጋር) ፋይዳ የሌለው ይመስል ነበር። ሆኖም እነዚህ ተከታታይ ነገሮች የቀድሞ ኪዳኖች መጣስ እንደሌለባቸው፣ በተለይም የፍጥረትን ሥርዐት በተመለከተ እንደ እግዚአብሔር ኪዳን ሆነው እንዲጠበቁና ለወደፊት በሚሆነውም ተሐድሶ ሁሉም እንደሚፈጸሙ ማረጋገጫ ይሰጣሉ።

*33፥17፤* 2ሳሙ7፥12-16፤ 1ነገ2፥4፤ 8፥25፤ 9፥5፤ 2ዜና 6፥16፤ 7፥12 ይመ። ይህ ክፍል በኢየሱስ ተፈጽሞአል (ሉቃ 1፥32-33 ይመ)።

*33፥18፤* ዘኍ25፥13 ይመ። ለሌዋውያን የተሰጠው የክህነት ቃል ኪዳን ለዳዊት እንደ ተሰጠው ንጉሣዊ ቃል ኪዳን የካህኑን ቤተ ሰብና ጌታን ብቻ የሚመለከት የግል ስጦታ አልነበረም። ይህም እስራኤል በጌታ ፊት ተቀባይነት ያለው የክህነት አገልግሎት እንዳላት ያወቀችበትና እግዚአብሔርም ከሕዝቡ ጋር የሠራበት ዋና ነገር ነው፤ በዚህ አማካይነትም ሕዝቡ ከጌታ ጋር ግንኙነት ያደርግ ነበር። አገልግሎቱም ከሁሉ የሚበልጥ የክህነት አገልግሎት በሰጠውና እየሰጠ ባለው በኢየሱስ ተፈጽሟል፤ እየተፈጸመም ነው (መዝ110፥4፤ ዕብ5፥6-10፤ 6፥19-20፤ 7፥11-25 ይመ)። *ሌዋውያን ከሆኑት ካህናትም፤* ዘዳ17፥9፡18 ይመ።

33፥20 *ለቀንና ለሌሊት ... ሥርዐት፤* ቍ25፤ 31፥35-36 ይመ። የእግዚአብሔርን ሉዓላዊ የሥነ ፍጥረት ሥርዐት አመሠራረት የሚያመለክት ቢሆንም፣ በዘፍ9፥8-17 ላይ (ዘፍ8፥22) ያለው ቃል ኪዳን ተገልጦአል።

33፥21 *ከሚያገለግሉት ሌዋውያን ጋር ... ኪዳን፤* ሚል 2፥4 ይመ።

*33፥22፤* ከነገድ አባቶች ጋር (በዘፍ22፥17 ከአብርሃም ጋር፣ በዘፍ26፥4 ከይስሐቅ ጋር በዘፍ32፥12 ከያዕቆብ ጋር) እግዚአብሔር የሰጣቸው የኪዳን ተስፋዎች በሚንጸባርቁባቸው ቃላት እነዚህ ሁለት የካህናት ቤተ ሰቦች (የካህናትና የነገሥታት) እንደ

እንደማይሰፈር የባሕር አሸዋ አበዛቸዋለሁ::’ ”

[23]የእግዚአብሔር ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [24]“ይህ ሕዝብ፣ ‘እግዚአብሔር፣ የመረጣቸውን ሁለቱን መንግሥታት[ፐ] ጥሎአል’ እንደሚሉ አላስተዋልህምን? ሕዝቤን ንቀዋል፤ እንደ ሕዝብም አልቈጠሯቸውም:: [25]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ‘የቀንና የሌሊት ኪዳኔን፣ የሰማይንና የምድርንም ሥርዐት ያጸናሁ እኔ ካልሆንሁ፣ [26]የያዕቆብንና የአገልጋዬን የዳዊትን ዘር እጥላለሁ፤ ከልጆቹም በአብርሃም፣ በይስሐቅና በያዕቆብ ዘር ላይ ገዥ እንዲሆኑ አልመርጥም፤ ይህንም የምለው ምርኮአቸውን ስለምመልስና[ሀ] ስለምራራላቸው ነው::’ ”

## ለሴዴቅያስ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

**34** የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደናፆርና ሰራዊቱ ሁሉ፣ በግዛቱም ሥር ያሉ መንግሥታትና ሕዝቦች ሁሉ ኢየሩሳሌምንና በአካባቢዋ የሚገኙትን ከተሞች ይወጉ በነበረ ጊዜ፣ እንዲህ የሚል ቃል ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ ኤርምያስ መጣ፤ [2]“የእስራኤል ስምላክ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ወደ ይሁዳ ንጉሥ ወደ ሴዴቅያስ ሄደህ እንዲህ ብለህ ንገረው፤ ‘እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ይህችን ከተማ ለባቢሎን ንጉሥ አሳልፌ ልሰጣት ነው፤ እርሱም በእሳት ያቃጥላታል፤ [3]አንተም በእርግጥ ትያዛለህ ዐልፈህም ለእርሱ ትሰጣለህ እንጂ ከእጁ አታመልጥም:: የባቢሎንን ንጉሥ በዐይኖችህ ታየዋለህ፤ ፊት ለፊትም ያነጋግርሃል፤ ወደ ባቢሎንም ትሄዳለህ::

[4]“ ‘ነገር ግን፣ የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ቃል ስማ፤ እግዚአብሔር ስለ አንተ እንዲህ ይላል፤ በሰይፍ አትሞትም፤ [5]በሰላም ትሞታለህ:: ሕዝቡ ከአንተ በፊት ለነበሩት ነገሥታት አባቶችህ ክብር በቀብራቸው ጊዜ እሳት እንዳነደዱ፣ በቀብርህም ጊዜ ስለ ክብርህ እሳት ያነዳሉ፤ “ዋይ ዋይ ጌታችን!” እያሉም ያለቅሱልሃል፤ እኔ ራሴ ይህን ቃል ተናግሬአለሁና፤ ይላል እግዚአብሔር::’ ”

[6]ነቢዩ ኤርምያስ ይህን ሁሉ ለይሁዳ ንጉሥ ለሴዴቅያስ በኢየሩሳሌም ነገረው፤ [7]በዚህም ጊዜ የባቢሎን ንጉሥ ሰራዊት ኢየሩሳሌምንና የቀሩትን የይሁዳ ከተሞች ለኪሶንና ዓዜቃን እየወጋ ነበር፤ ከተመሸጉት የይሁዳ ከተሞችም የቀሩት እነዚሁ ብቻ ነበሩና::

## የባሪያዎች ነጻ አለመውጣት

[8]ንጉሡ ሴዴቅያስ ባሪያዎችን ነጻ ለማውጣት ከኢየሩሳሌም ሕዝብ ሁሉ ጋር ቃል ኪዳን ካደረገ በኋላ፣ የእግዚአብሔር ቃል ወደ ኤርምያስ መጣ:: [9]እያንዳንዱ ሰው፣ ዕብራዊ የሆነውን ወንድ ባሪያውንና

[ፐ]24 ወይም ወገን
[ሀ]26 ወይም ከምርኮ እመልሳቸዋለሁ

33፥24 ነሀ4፥4፤ኤር30፥17፤ሕዝ36፥20፤37፥22
33፥25 ዘፍ1፥8፤መዝ74፥16-17፤148፥6
33፥26 ቍ7፤ዘሌ26፥44፤መዝ14፥7፤ኢሳ14፥1፤ኤር30፥18
34፥1 2ነገ25፥1፤ኤር27፥7፤39፥1
34፥2 ቍ22፤2ዜና36፥11፤ኤር32፥29፤37፥8
34፥3 2ነገ25፥7፤ኤር21፥7
34፥4 ኤር52፥11
34፥5 2ዜና16፥14፤ኤር22፥18
34፥7 ኢሱ10፥3:10፤2ዜና11፥9
34፥8 ዘፀ21፥2፤ዘሌ25፥10:39-41፤2ነገ11፥17፤ነሀ5፥5-8
34፥9 ዘዳ15፥12-18

ሚያድጉና ይህም አገልግሎት ከሕዝቡ ጋር በመሠረተው መንፈሳዊ ኅብረት እየተስፋፋ እንደሚሄድ ጌታ አረጋግጦአል:: ይህ በሁለቱ ቤት ሰቦች በኩል ለተለያዩ ትውልዶች የተሰጠው ተስፋ ከክርስቶስ ጋር በሚነግሡት ሕዝቦች በኩል ሙሉ በሙሉ ተፈጻሚነት እንደሚያገኝ አያጠራጥርም (ሮሜ5፥17፤8፥17፤ 1ቆሮ6፥3፤ 2ጢሞ 2፥12፤ ራእ3፥21፤ 5፥10፤ 20፥5-6፤ 22፥5 እንዲሁም ማቴ 19፥28፤ ሉቃ22፥30 ይመ)፤ በክርስቶስ በኩል ካህናት ለመሆን በተጠሩትም አማካይነት ይፈጸማል (1ጴጥ2፥5፡9፤ ራእ1፥6፤ 5፥10፤ 20፥6 እንዲሁም ኢሳ 66፥21፤ ሮሜ 6፥13፤ 12፥1፤ 15፥16፤ ኤፌ 5፥2፤ ፊል4፥18፤ ዕብ13፥15-16 ይመ)::

33፥24 *ሁለቱን መንግሥታት፤* እስራኤልንና ይሁዳን ማለት ነው:: እዚህ ላይ የሚተካው የዕብራይስጥ ቃል ቤተ ሰብን ለማመልከት የሚጠቅም የተለመደ ቃል ሲሆን፣ ይህም የካህናቱንና የነገሥታትን ቤተሰብ ወይም የያዕቆብንና የዳዊትን (ቍ26 ይመ) ሳያመለክት አይቀርም፤ *የመረጣቸውን፤* አሞ3፥2 እና ማብ ይመ::

*33፥25-26፤* ቍ20 እና ማብ ይመ::

33፥26 *ምርኮአቸውን ስለምመልስና ስለምራራላቸው፤* ዘዳ30፥3 ላይ ያለውን ያስስባል:: የ29፥14 ማብ ይመ::

*34፥1-35፥19፤* እዚህ ላይ የመጽሐፉ የመጀመሪያው ዋና ክፍል (ም2-35) ሊያልቅ እየተቃረበ ነው:: ኤርምያስ ለይሁዳ የሚሰጠውን ማስጠንቀቂያና የሚያቀርበውን ልመና የሚደመድመው ታሪካዊ ይዘት ባለው ተጨማሪ ሐሳብ ነው (ም34-35)፤ ይህም የመጽሐፉን ሦስተኛ ዋና ክፍል (ም39-45) እንዲሁም (የ45፥1-5 ማብ ይመ) በኤርምያስ ሳይሆን፣ በሌላ ሰው የተጻፈውና ከዳር እስከ ዳር ለመጽሐፉ የሚስማማ ታሪካዊ ይዘት ኖሮት የተጨመረውን ም52ን ለማጠቃለል (ለመደምደም) የሚጠቅም ዘዴ ነው::

*34፥1-22፤* ይህ መጽሐፍ በሁለት ይከፈላል (ከቍ1-7 እና ከቍ8-22)፤ እያንዳንዱ ክፍል የተጻፈው በ588 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው (የቍ7፥21-22 ማብ ይመ)::

*34፥1-7፤* ኤርምያስ ለንጉሥ ሴዴቅያስ የተናገረው ማስጠንቀቂያ፣ በ21፥1-10 ላይ ከተሰጠው ተግሣጽ ጋር ይመሳሰላል (የዚያኑ ማብ ይመ)::

34፥1 *በግዛቱም ሥር ያሉ መንግሥታትና ሕዝቦች፤* የናቡከደነፆር ግዛት እጅግ ሰፊ ነበር (ሕዝ26፥7፤ ዳን3፥2-4፤ 4፥1 ይመ፤ በ51፥28 ላይ ስለ ሜዶን ከተሰጠው ተመሳሳይ ገለጻ ጋር ያነጻጽሩ):: *ኢየሩሳሌም ... ይወጉ በነበረ ጊዜ፣* ቅኝ ተገዥዎች የነበሩ አገሮች ገዢቸው ከሆነው መንግሥት ጐን ተሰልፈው እንዲዋጉ ወታደሮቻቸውን መላክ ግዴታቸው ነበር (2ነገ24፥2 ይመ):: *በአካባቢዋ የሚገኙትን ከተሞች፤* 19፥15 እና ማብ ይመ::

*34፥2-3፤* 32፥3-5 እና ማብ፤ እንዲሁም 39፥4-7፤ ሕዝ 12፥12፤ 17፥11-20 ይመ::

34፥4 *በሰይፍ አትሞትም፤* 32፥5፤ 38፥17:20፤52፥11፤ሕዝ 17፥16 ይመ::

34፥5 *... በፊት ለነበሩት ነገሥታት ... ክብር በቀብራቸው ጊዜ እሳት እንዳነደዱ፤* በድኑን ለማቃጠል አይደለም (2ዜና 16፥14፤ 21፥19 እንዲሁም የአሞ6፥10 ማብ ይመ):: *ዋይ ዋይ ጌታችን፤* ንጉሥ ሲሞት ሐዘንን ለመግለጽ የሚነገር ቃል ነው (22፥18 ይመ፤ ከ1ነገ13፥30 ጋር ያነጻጽሩ)::

34፥7 *ለኪሶንና ዓዜቃን፤* እነዚህን ከተሞች የሠራቸው የሰሎሞን ልጅ ሮብዓም ነው (2ዜና11፥5:9 ይመ)፤ በኋላ ግን ለኪሶ በሕዝቅያስ ዘመነ መንግሥት በአሦር ንጉሥ በሰናክሬም (2ዜና32፥9) ተከበበች (በ701 ዓ.ቅ.ክ):: ስለ ድል የሚገልጸው በዚያ ጊዜ የተሠራውና የሰናክሬምን ድል የሚገልጸው ቅርጽ፣ ንጉሡ በዙፋን ላይ ተቀምጦ ከለኪሶ የተበዘበዘውን ምርኮ በመመርመር ጊዜ ማሳለፉን ያሳያል:: በ1935 ዓ.ም እንደ ብራና እንደ ወረቀት ሁሉ ለመጻፊያ የሚያገለግሉ ዐሥራ ስምንት የሸክላ ስባሪዎች በለኪሶ ተገኝተዋል፤ እነዚህ ሁሉ የወጡት ከእስራኤላውያን የበር ማማ ፍርስራሽ ውስጥ ነው::

*34፥8-22፤* በ37፥4-12 ላይ ከተጠቀሰው ድርጊት ጋር በተመሳሳይ ጊዜ ተፈጸመ (የቍ21-22 ማብ ይመ)::

34፥8 *ነጻ ለማውጣት፤* ዘሌ25፥10 እና ማብ ይመ:: *ባሪያዎችን ነጻ ለማውጣት፤* የሚፈጸመውም በሙሴ ሕግ መሠረት ነው (ዘፀ21፥2-11 እና ማብ፤ ዘሌ25፥39-55፤ዘዳ15፥12-18 ይመ)::

34፥9 *ዕብራዊ፤* ዘፀ 21፥2፤ የዘፍ 14፥13 ማብ ይመ::

ዕብራዊት የሆነችውን ሴት ባሪያውን ነጻ ማውጣት ነበረበት፤ ማንም ሰው አይሁዳዊ ወንድሙን በባርነት መግዛት አልነበረበትም:: [10]በዚህ ቃል ኪዳን የተስማሙት ባለሥልጣኖችና ሕዝቡ ሁሉ ወንድ ወይም ሴት ባሪያዎቻቸውን ነጻ ለመልቀቅና ከእንግዲህ ባሪያ አድርገው ላይገዟቸው ተስማሙ:: [11]በኋላ ግን ሐሳባቸውን ቀይረው ነጻ የለቀቋቸው ባሪያዎቻቸውን እንዲመለሱ አደረጓቸው፤ እንደገናም ባሪያ አድርገው ገዟቸው::

[12]ስለዚህ *የእግዚአብሔር ቃል* ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል *መጣ*፤ [13]"የእስራኤል አምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በባርነት ከተገዙበት ከግብፅ ምድር ባወጣኋቸው ጊዜ፣ ከአባቶቻችሁ ጋር እንዲህ ብዬ ቃል ኪዳን አደረግሁ፤ [14]'ራሱን በባርነት ለእናንተ የሸጠውን ዕብራዊ ወንድማችሁን እያንዳንዳችሁ በየሰባት ዓመቱ ነጻ ትለቃላችሁ፤ ስድስት ዓመት ከተገዛላችሁ በኋላ ነጻ ታወጡታላችሁ::'[a] አባቶቻችሁ ግን አልሰሙኝም ጆሮአቸውንም ወደ እኔ አላዘነበሉም:: [15]እናንተም አሁን ንስሓ በመግባት በፊቴ ትክክለኛ ነገር አደረጋችሁ፤ እያንዳንዳችሁም ለወገኖቻችሁ ነጻነት ዐወጃችሁ፤ ስሜ በሚጠራበት ቤትም በፊቴ ቃል ኪዳን ገባችሁ:: [16]ነገር ግን ተመልሳችሁ ስሜን አረከሳችሁ፤ ወደ ፈለጉበት እንዲሄዱ ነጻ የለቀቃችኋቸውንም ወንዶችና ሴቶች ባሪያዎቻችሁን መለሳችሁ፤ እንደ ገናም ባሪያዎቻችሁ አደረጋችኋቸው::

[17]"ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ለወንድሞቻችሁና ለወገኖቻችሁ ነጻነት አላወጃችሁምና አልታዘዛችሁኝም:: እንግዲህ እኔ 'ነጻነት' ዐውጅላችኋለሁ፤ ይላል *እግዚአብሔር*:: ይኸውም በሰይፍ፣ በቸነፈርና በራብ የምትወድቁበት 'ነጻነት' ነው:: ለምድር መንግሥታት ሁሉ መሠቀቂያ አደርጋችኋለሁ:: [18]ኪዳኔን ያፈረሱትንና በፊቴ የገቡትን የኪዳኑን ቃል ያልፈጸሙትን ሰዎች ሥጋውን ሁለት ቦታ ከፍለው በመካከሉ እንዳለፉት፣ እንደ እንቦሳው አደርጋቸዋለሁ:: [19]የይሁዳንና የኢየሩሳሌምን መሪዎች፣ የቤተ መንግሥቱን ባለሟሎች፣ ካህናቱንና በእንቦሳው ሥጋ መካከል ያለፉትን ሕዝብ ሁሉ፣ [20]ነፍሳቸውን ለሚሹ ጠላቶቻቸው አሳልፌ እሰጣለሁ፤ ሬሳቸውም ለሰማይ ወፎችና ለምድር አራዊት መብል ይሆናል::

[21]"የይሁዳን ንጉሥ ሴዴቅያስንና መኳንንቱን፣ ነፍሳቸውን ለሚሹ ጠላቶቻቸው ይኸውም ለጊዜው እናንተን ከመውጋት ለተመለሱ ለባቢሎን ንጉሥ ሰራዊት አሳልፌ እሰጣለሁ:: [22]እነሆ፤ አዛቸዋለሁ፤ ይላል *እግዚአብሔር*፤ ወደዚህችም ከተማ እንደ ገና እመልሳቸዋለሁ:: እነርሱም ይወጓታል፤ ይይዟታል፤ በእሳትም ያቃጥሏታል:: የይሁዳንም ከተሞች ሰው የማይኖርባቸው፣ ባድማ አደርጋቸዋለሁ::

## የሬካባውያን ታማኝነት

**35** በይሁዳ ንጉሥ በኢዮስያስ ልጅ፣ በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት፣ *ከእግዚአብሔር* ዘንድ እንዲህ የሚል ቃል ወደ ኤርምያስ *መጣ*፤ [2]"ወደ ሬካባውያን ሂደህ ወደ *እግዚአብሔር* ቤት አምጣቸው፤ ወደ አንዱም ክፍል አስገብተህ የሚጠጡትን ወይን ጠጅ ስጣቸው::"

[a]14 ዘዳ 15፥12

34፥11 መዝ78፥37
34፥13 ዘፀ24፥8፤ ዘዳ15፥15
34፥14 ዘፀ21፥2፤ 2ነገ17፥14፤ኤር 7፥26
34፥15 ቍ-8፤ኤር 32፥24
34፥16 ዘሌ19፥12 ፤ሕዝ3፥20፤18፥24
34፥17 ኤር14፥12፤ 15፥4፤21፥7፤24፥9፤ 29፥18፤ማቴ7፥2፤ገላ 6፥7
34፥18 ዘፍ15፥10፤ ኤር11፥10
34፥19 ኤር26፥10፤ ሶፎ 3፥3-4
34፥20 ዘዳ28፥26፤ ኤር11፥21፤21፥7፤ ሕዝ16፥27፤23፥28
34፥21 2ነገ25፥21፤ 2ዜና36፥10፤ኤር 21፥7፤32፥4፤ 37፥5፤ 39፥6፤52፥24-27
34፥22 ዘሌ26፥32፤ ነህ2፥17፤ኢሳ 1፥7፤ ኤር38፥18፤39፥1-2፡ 8፤ሕዝ23፥47
35፥1 2ዜና36፥5
35፥2 1ነገ 6፥5፤ 2ነገ10፥15

*ማንም ... ወንድሙን በባርነት መግዛት አልነበረበትም፤* ዘሌ 25፥39፡42 ይመ::

34፥10 *ባሪያ አድርገው ላይገዟቸው፤* ይህን ያደረጉት ከእግዚአብሔር በረከት ለመቀበልና ወይም ነጻ የወጡት ባሪያዎች ኢየሩሳሌምን በመጠበቅ ተግባር ውስጥ ለመሳተፍ የበለጠ ፈቃደኞች እንደሚሆኑ ተስፋ በማድረግ ነው::

34፥11 *በኋላ ግን፤* ከግብፅ ጣልቃ ገብነት የተነሣ (ቍ21-22፤37፥5፡11 ይመ) የባቢሎናውያን ከበባ ለጊዜው ቆም ብሎ በነበረበት ጊዜ:: *ነጻ የለቀቋቸው ባሪያዎቻቸውን እንዲመለሱ አደረጓቸው፤* ይህም በዘዳ15፥12 ላይ የተጻፈውን ሐሳብ በመሻር ነው:: *ባሪያ አድርገው ገዟቸው፤* ከ2ዜና28፥10 ጋር ያነጻጽሩ::

34፥13 *በባርነት ከተገዙበት ከግብፅ ምድር፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "የባሮች ቤት" ማለት ነው (ዘፀ13፥3፡14፤ 20፥2፤ ዘዳ5፥6፤ 6፥12፤ 8፥14፤ 13፥5፤ ኢያ24፥17፤ መሳ6፥8 ይመ):: እግዚአብሔር ከዚያ በፊት እስራኤላውያንን ከባርነት ነጻ ስላወጣቸው፣ (ዘዳ15፥15) እነርሱም እንዲሁ ባሮቻቸውን ነጻ መልቀቅ ነበረባቸው::

34፥14 *በየሰባት ዓመቱ ነጻ ትለቃላችሁ፤* በዘዳ15፥12 ላይ የተጻፈውን ሐሳብ በከፊል ይዞአል::

34፥15-16 *ንስሓ በመግባት ... ተመልሳችሁ፤* ሁለቱንም ሐረግ የሚገልጸው የዕብራይስጥ ቃል አንድ ዐይነት ሲሆን፣ በውስጡ ምፀታዊ የቃላት ጨወታ ይዟል (የቍ18 ማብ ይመ)::

34፥16 *ስሜን አረከሳችሁ፤* የእግዚአብሔርን ኪዳን በማፍረስ ነው:: ሴዴቅያስ ቃሉ የማይታመን ሰው ነበር (ሕዝ17፥15፡18 ይመ):: *ወደ ፈለጉበት እንዲሄዱ፤* ዘዳ21፥14 ይመ::

34፥17 *በሰይፍ፣ በቸነፈርና በራብ፤* የ14፥12 ማብ ይመ:: *ለምድር መንግሥታት ሁሉ መሠቀቂያ፤* 15፥4 እና ማብ ይመ::

34፥18 *ሁለት ቦታ ከፍለው፤* የዘፍ15፥17 ማብ ይመ::

34፥20 *ለሰማይ ወፎችና ለምድር ... መብል፤* 7፥33 እና ማብ ይመ::

*34፥21-22፤* ግብፃውያን፣ እስራኤላውያንን ለመርዳት በመምጣታቸው፣ በ588ዓ.ቅ.ክ ላይ ባቢሎናውያን የኢየሩሳሌምን ከበባ ለጊዜው ተወት አደረጉት (የቍ11 ማብ ይመ)::

34፥21 *እናንተን ... ለተመለሱ፤* በ21፥2 ላይ የተገለጸውን ተስፋ ይመ::

34፥22 *እንደ ገና እመልሳቸዋለሁ፤* 37፥8 ይመ::

*35፥1-19፤* የቀድሞ አባታቸውን ትዕዛዝ የፈጸሙት የሬካባውያን ቤተሰብ፣ ለእግዚአብሔር ላልታዘዘው ለይሁዳ ሕዝብ (ቍ16) ምሳሌና የመነቀፊያ ምክንያት ናቸው:: በቍ11 ላይ የባቢሎንና የሶርያ ሰራዊት መጠቀሱ ይህ ምዕራፍ የተጻፈው ከንጉሥ ኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት ስምንተኛ ዓመት በፊት እንዳልሆነ ያመለክታል:: የኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት የጀመረው በ609ዓ.ቅ.ክ ላይ ሲሆን፣ በነገሠ ከሦስት ወይም ከአራት ዓመት በኋላ በናቡከደነፆር ላይ ዐመፀ፤ ይህ ዐመፅ ባቢሎናውያንን፣ ሶርያውያንንና ሌሎችንም ግዛቱን እንዲወሩ ስለ አነሣሣቸው፣ አድራጎቱ ማስተዋል የጐደለው ነበር (2ነገ24፥1-2 ይመ፤ በ12፥7-10 ላይ የተጠቀሰው ሐሳብ ወረራውን ያንጸባርቃል):: በ605 ዓ.ቅ.ክ ላይ ዋና ከተማው ኢየሩሳሌም ተከበበች (ዳን1፥1 እና ማብ ይመ)::

35፥1 *በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት፤* ም35-36 (36፥1 ይመ) ከ609-598 ዓ.ቅ.ክ የነበረውን ያስታውሳል::

35፥2 *ሬካባውያን፤* ከቄናውያን ጋር ዝምድና ያላቸው (1ዜና2፥55) ዘላን ጐሣዎች ናቸው፤ ከእነዚህም ጥቂቶቹ በእስራኤል መካከል ወይም አቅራቢያ ከመኖራቸውም በላይ (መሳ1፥16፤ 4፥11፤1ሳሙ27፥10 ይመ)፤ ከእነርሱ ጋር መልካም ግንኙነት ነበራቸው (1ሳሙ 15፥6፤ 30፥26፡29ይመ):: *ወደ እግዚአብሔር ቤት ... ወደ አንዱም ክፍል፤* ለዕቃ ማስቀመጫ ወይም ለመኖሪያ ያገለግል የነበረ ክፍል ነው (1ነገ6፥5፤ 1ዜና28፥12፤ 2ዜና31፥11፤ ነህ 13፥4-5 ይመ)::

[3]ስለዚህ የካባስን ልጅ የኤርምያስን ልጅ ያእዛንያን፣ ወንድሞቹንና ወንዶች ልጆቹን ሁሉ፣ የሬካባውያንን ወገን በአጠቃላይ ሄጄ ጠራኋቸው፤ [4]ወደ *እግዚአብሔር* ቤት አመጣኋቸው፤ ወደ ሐናን ልጆች ክፍልም አስገባኋቸው፤ የሐናን አባት ጌዴልያም *የእግዚአብሔር* ሰው ነበረ:: ክፍሉም በመኳንንቱ ክፍል አጠገብ፣ ከመዕሤያ ክፍል በላይ ነበር፤ መዕሤያም የበር ጠባቂው የሰሎም ልጅ ነበረ፤ [5]በሬካባውያንም ሰዎች ፊት በወይን ጠጅ የተሞሉ ማድጋዎችን አቀረብሁ፤ ዋንጫዎችንም ሰጥቻቸው፣ "ብሉ፤ የወይን ጠጅ ጠጡ" አልኋቸው::

[6]እነርሱ ግን እንዲህ አሉ፤ "የወይን ጠጅ አንጠጣም፤ አባታችን የሬካብ ልጅ ኢዮናዳብ እንዲህ ብሎ አዝዞናል፤ 'እናንተና ዘራችሁ ከቶ የወይን ጠጅ አትጠጡ፤ [7]ቤት አትሥሩ፤ ዘር አትዝሩ፤ ወይን አትትከሉ፤ ሁልጊዜ በድንኳን ኑሩ እንጂ ከእነዚህ ነገሮች አንዱም አይኑራችሁ፤ ይህም ሲሆን እንደ መጻተኛ በሆናችሁበት ምድር ረዥም ዘመን ትኖራላችሁ::' [8]እኛም አባታችን የሬካብ ልጅ ኢዮናዳብ ያዘዘንን ሁሉ ፈጽመናል፤ እኛና ሚስቶቻችን፣ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻችንም የወይን ጠጅ ጠጥተን አናውቅም፤ [9]የምንቀመጥበትም ቤት አልሠራንም፤ የወይን ቦታ፣ የዕርሻ ስፍራ ወይም የእህል ዘር የለንም:: [10]በድንኳን ኖረናል፤ አባታችን ኢዮናዳብ ያዘዘንንም ሁሉ ጠብቀናል:: [11]ነገር ግን የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደናፆር ይህችን ምድር በወረረ ጊዜ፣ 'ኑ፤ ከባቢሎን[*] ሰራዊትና ከሶርያ ሰራዊት ሸሽተን ወደ ኢየሩሳሌም እንሂድ' ተባባልን፤ ስለዚህም በኢየሩሳሌም ተቀመጥን::" [12]*የእግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [13]"የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ሂድ፤ ለይሁዳ ሰዎችና ለኢየሩሳሌም ሕዝብ እንዲህ ብለህ ተናገር፤ 'ቃሌን ትጠብቁ ዘንድ ከዚህ አትማሩምን?' ይላል *እግዚአብሔር*፤ [14]'የሬካብ ልጅ ኢዮናዳብ ልጆቹ የወይን ጠጅ እንዳይጠጡ አዘዛቸው፤ ይህም ትእዛዝ ተጠብቆአል፤ የአባታቸውን ትእዛዝ ስለ ጠበቁ እስከ ዛሬ ድረስ የወይን ጠጅ አይጠጡም፤ እናንተ ግን እኔ ደጋግሜ ብናገራችሁም፤ አልታዘዛችሁኝም:: [15]አገልጋዮቼን ነቢያትን ሁሉ ደጋግሜ ወደ እናንተ ላክሁ፤ እነርሱም፣ "እያንዳንዳችሁ ከክፉ መንገዳችሁ ተመለሱ፤ ምግባራችሁን አስተካክሉ፤ ለእናንተና ለአባቶቻችሁ በሰጠኋቸው ምድር ትኖሩ ዘንድ ሌሎቹን አማልክት ለማገልገል አትከተሉ" አልኋችሁ:: እናንተ ግን ጆሮአችሁን ወደ እኔ አላዘነበላችሁም፤ አልሰማችሁኝምም:: [16]የሬካብ ልጅ የኢዮናዳብ ዘሮች አባታቸው የሰጣቸውን ትእዛዝ ጠብቀዋል፤ ይህ ሕዝብ ግን አልታዘዘኝም::'

[17]"ስለዚህ የእስራኤል ስምባክ፤ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'እነሆ፤ በይሁዳና በኢየሩሳሌም በሚኖሩት ሁሉ ላይ አደርሳለሁ ያልሁትን ጥፋት ሁሉ አመጣባቸዋለሁ፤ በተናገርኋቸው ጊዜ፣ አልሰሙኝምና በጠራኋቸውም ጊዜ አልመለሱልኝም::' "

[18]ኤርምያስም ሬካባውያንን እንዲህ አላቸው፤ "የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'የአባታችሁን የኢዮናዳብን ትእዛዝ ስለ ጠበቃችሁ፤ መመሪያውን ስለ ተከተላችሁ፤ ያዘዛችሁንም ሁሉ ስለ ፈጸማችሁ' [19]የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ከሬካብ ልጅ ከኢዮናዳብ ወገን የሚያገለግለኝ ሰው ለዘላለም አይታጣም::' "

[*]11 ወይም *ከለዳውያን*

35፥4 ዘጸ33፥1፤ 2ነገ12፥9፤23፥4፤ 1ዜና9፥19
35፥6 ዘሌ10፥9፤ ዘኍ6፥2-4፤2ነገ 10፥15፤ሉቃ1፥15
35፥7 ዘፀ20፥12፤ ኤፌ6፥2-3፤ዕብ11፥9
35፥8 ምሳ1፥8፤ቆላ 3፥20
35፥9 1ጢሞ6፥6
35፥11 ኢሱ10፥20፤ 2ነገ24፥1፤ኤር8፥14
35፥13 ኤር6፥10፤ 11፥6፤23፥33
35፥14 ቍ6-10፡16 ፤ኢሳ30፥9፤ኤር7፥13
35፥15 ዘፀ20፥3፤ ዘዳ4፥40፤2ነገ17፥13፤ ኢሳ1፥16-17፤59፥20፤ ኤር4፥1፤6፥10፤7፥25፡ 26፤18፥11፤25፥5፤ 26፥3፤ 44፥4-5፤ሕዝ 14፥6፤18፥30
35፥16 ዘሌ20፥9፤ ሚል1፥6
35፥17 ኢሱ23፥15፤ 1ነገ13፥34፤ምሳ1፥24 ፤ኤር7፥13፤21፥4-7፤ ሮሜ10፥21
35፥18 ዘፍ31፥35
35፥19 ኢሳ48፥19፤ ኤር15፥19፤33፥17

35፥3 *ያእዛንያ*፣ ትርጉሙ፣ "እግዚአብሔር ይሰማል" ማለት ነው፤ በኤርምያስ ዘመን የተለመደ ስም ነበር (40፥8፤ ሕዝ 8፥11፤ 11፥1 ይመ)፤ ይህ ስም በማኅተም ላይ ከመቀረጹም በላይ በለኪሶ በድንጋይ ላይ ተጽፈው ከተገኙት ጽሑፎች መካከልም በአንዱ ላይ ተገኝቶአል (የ34፥7 ማብ ይመ):: *ኤርምያስ*፣ ይህ ሰው ነቢዩ ኤርምያስ አይደለም::

35፥4 *ልጆች*፤ ደቀ መዛሙርት ከመሆን አቅጣጫ የተባለ ሊሆን ይችላል (አሞ7፥14 እና ማብ ይመ):: *የእግዚአብሔር ሰው*፣ 'ነቢይ' ከሚለው ጋር ተመሳሳይ ሲሆን (1ነገ12፥22 እንዲሁም የ1ሳሙ9፥9 ማብ ይመ)፣ ከጠራው ጋር ያለውን ግንኙነትና ቅርበት ያመለክታል:: *መዕሤያም*፤ በ21፥1፤ 29፥25፤ 37፥3 ላይ በዚህ ስም የተጠራው ሰው ሊሆን ይችላል:: *የበር ጠባቂው*፣ የመቅደሱን መግቢያ በር ይጠብቁ የነበሩትን ዘበኞች (2ነገ12፥9 ይመ) ከሚቈጣጠሩት ከሦስቱ ሰዎች አንዱ (52፥24 ይመ) ነው::

35፥5 *ማድጋዎችን*፤ ብዙ ትናንሽ ዋንጫዎችን ሊሞሉ የሚችል ትልልቅ ዕቃዎች ናቸው::

35፥6 *የወይን ጠጅ አንጠጣም*፤ ሬካባውያን ምን ጊዜም የማያፈርሱት ቃል ኪዳን ነው:: ናዝራውያን ለተወሰነ ጊዜ ሊፈጽሙት ከሚገባ ቃል ኪዳን ጋር ያነጻጽሩ (ዘኍ6፥2-3፡20፤ መሳ 13፥4-7 ይመ):: የሬካብ ልጅ መልክያ፣ «የወይን ተክል እርሻ ቤት» የሚል ትርጉም ያለው የቤትሐካሪም ግዛት አለቃ ስለ ነበር (ነሀ3፥14)፣ የሬካባውያንን ቃል ኪዳን የማያከብር ኋላ ላይ የመጣ ሊሆን ይችላል:: *ኢዮናዳብ*፣ ኤርምያስ ከነበረበት ሁለት መቶ አምሳ ዓመት ያህል በፊት የበኣልን አምልኮ ከሰሜኑ መንግሥት ለማጥፋት ንጉሥ ኢዩን ለተወሰነ ጊዜ የረዳ ሰው ነው::

35፥7 *ሁልጊዜ በድንኳን ኑሩ*፤ የአስቸኳይ ጊዜ ሁኔታ ካልተፈጠረ በስተቀር የሚኖሩት እንደዚህ ነው (ቍ11 ይመ):: ... *ምድር ረዥም ዘመን ትኖራላችሁ*፤ አንድ ሰው የወላጆቹን ትእዛዝ ማክበር እንደሚገባው የሚያመለክተውን የዘፀ20፥12 ሐሳብ የሚያንፀባርቅ ነው::

35፥8 ... *ኢዮናዳብ ያዘዘንን ሁሉ ፈጽመናል*፤ ይሁዳ በእግዚአብሔር ፊት ካሳየው አለመታዘዝ ጋር ያነጻጽሩ (ቍ16 ይመ)::

*35፥11*፤ የቍ1-19 ማብ ይመ::

35፥13 *አትማሩምን?* ይህን ሐሳብ የሚገልጸው የዕብራይስጥ ቃል በ2፥3 እና በ7፥28 ላይ "ተግሣጽን አልተቀበሉም" ተብሎ ተተርጒሞአል (5፥3፤ 17፥23 እና ማብ ይመ)::

35፥14-15 *ደጋግሜ*፤ የ7፥13 ማብ ይመ::

*35፥17*፤ 11፥11 ይመ::

35፥19 *የሚያገለግለኝ ሰው ለዘላለም አይታጣም*፣ 33፥18 ይመ:: ከባቢሎን ምርኮ መልስ በተከናወነው የኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ ግንባታ ውስጥ ሬካባውያን ሊወጡት የሚገባቸው የተለየ ኀላፊነት ዘግየት ብሎ የተሰጣቸው መሆኑ በአይሁድ ሚሽና ላይ ተገኝቷል::

*36፥1-38፥28*፤ እነዚህ ሦስት ምዕራፎች የኤርምያስን መከራና ስደት በተመለከተ የያዙት ፍሬ ሐሳብ ተመሳሳይ ስለ ሆነ ተቀራራቢ ናቸው::

*36፥1-32*፤ በዚህ ክፍል ንጉሥ ኢዮአቄም ኤርምያስ

## ኢዮአቄም የኤርምያስን ብራና አቃጠለ

**36** የይሁዳ ንጉሥ የኢዮስያስ ልጅ የነበረው ኢዮአቄም በነገሠ በአራተኛው ዓመት እንዲህ የሚል ቃል ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ ኤርምያስ መጣ፤ [2]“የብራና ጥቅልል ውሰድ፤ ለአንተም መናገር ከጀመርሁበት ከኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት አንሥቶ እስካሁን ድረስ ስለ እስራኤል፣ ስለ ይሁዳና ስለ ሌሎች ሕዝቦች ሁሉ የነገርሁህን ቃል ሁሉ ጻፍበት፤ [3]ምናልባትም የይሁዳ ሕዝብ ላመጣባቸው ያሰብሁትን ጥፋት ሁሉ ሲሰሙ፣ እያንዳንዳቸው ከክፉ መንገዳቸው ይመለሱ ይሆናል፤ እኔም ክፋታቸውንና ኀጢአታቸውን ይቅር እላለሁ።”

[4]ኤርምያስም የኔርያን ልጅ ባሮክን ጠራው፤ ባሮክም እግዚአብሔር የተናገረውን ቃል ሁሉ ከኤርምያስ አፍ ተቀብሎ በብራናው ላይ ጻፈ። [5]ኤርምያስም ባሮክን እንዲህ አለው፤ “እኔ ተከልክያለሁና ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ መግባት አልችልም፤ [6]ስለዚህ ወደ እግዚአብሔር ቤት ሄደህ፣ በቃል እየነገርሁህ በብራናው ላይ የጻፍኸውን የእግዚአብሔርን ቃል በጾም ቀን ለተሰበሰበው ሕዝብ አንብብ፤ ከየከተሞቻቸው ለመጡት ለይሁዳ ሕዝብ ሁሉ አንብብ። [7]እግዚአብሔር በዚህ ሕዝብ ላይ የተናገረው ቍጣና መቅሠፍት ታላቅ ስለ ሆነ፣ ምናልባት ልመናቸውን በእግዚአብሔር ፊት በማቅረብ እያንዳንዳቸው ከክፉ መንገዳቸው ይመለሱ ይሆናል።”

[8]የኔርያ ልጅ ባሮክ ነቢዩ ኤርምያስ የነገረውን ሁሉ አደረገ፤ በእግዚአብሔርም ቤተ መቅደስ የእግዚአብሔርን ቃል ከብራናው አነበበ። [9]የይሁዳ ንጉሥ የኢዮስያስ ልጅ የሆነው ኢዮአቄም በነገሠ በአምስተኛው ዓመት በዘጠነኛው ወር በኢየሩሳሌም የሚኖረው ሕዝብ ሁሉና ከይሁዳ ከተሞች የመጡት ሰዎች በእግዚአብሔር ፊት ጾም ዐወጁ። [10]ባሮክም በብራና ላይ የተጻፈውን የኤርምያስን ቃል በእግዚአብሔር ቤት በላይኛው አደባባይ፣ ‘አዲሱ በር’ በሚባለው በቤተ መቅደሱ መግቢያ ላይ በሚገኘው በጸሓፊው በሳፋን ልጅ በገማርያ ክፍል ውስጥ ሆኖ ለሕዝቡ ሁሉ አነበበው።

[11]የሳፋን ልጅ የገማርያ ልጅ ሚክያስ ከብራናው የተነበበውን የእግዚአብሔርን ቃል ሁሉ በሰማ ጊዜ፣ [12]በቤተ መንግሥቱ ውስጥ ወዳለው ወደ ጸሓፊው ክፍል ወረደ፤ በዚያም መኳንንቱ ሁሉ፦ ጸሓፊው ኤሊሳማ፣ የሸማያ ልጅ ድላያ፣ የዓክቦር ልጅ ኤልናታን፣ የሳፋን ልጅ ገማርያ፣ የሐናንያ ልጅ ሴዴቅያስ እንዲሁም ሌሎች መኳንንት ሁሉ ተቀምጠው ነበር። [13]ባሮክ ለሕዝቡ ከብራናው ሲያነብ ሚክያስ የሰማውን ሁሉ ከነገራቸው በኋላ፣ [14]መኳንንቱ ሁሉ የኩሲን ልጅ የሴሌምያን ልጅ የናታንያን ልጅ ይሁዲን፣ “ለሕዝቡ ያነበብኸውን ብራና ይዘህ እንድትመጣ” ብለው ወደ ባሮክ ላኩ። የኔርያም ልጅ ባሮክ ብራናውን ይዞ ወደ እነርሱ መጣ፤ [15]እነርሱም፣ “እስቲ ተቀምጠህ አንብብልን” አሉት። ባሮክም አነበበላቸው፤ [16]እነርሱም ቃሉን ሁሉ በሰሙ ጊዜ እርስ በርሳቸው በፍርሀት በመተያየት ባሮክን፣ ይህን ሁሉ ቃል ለንጉሡ መንገር ይገባናል።” አሉት፤ [17]ደግሞም፣ “ይህን ሁሉ እንዴት ልትጽፍ እንደ ቻልህ ንገረን፤ ኤርምያስ በቃል እየነገረህ ነውን?” ብለው ባሮክን ጠየቁት።

[18]ባሮክም፣ “አዎን ይህን ሁሉ በቃሉ ነገረኝ፤ እኔም በብራናው ላይ በቀለም ጻፍሁ” ብሎ መለሰላቸው።

[19]መኳንንቱም ባሮክን፣ “እንግዲያውስ አንተና ኤርምያስ ሄዳችሁ ተሸሸጉ፤ የት እንዳላችሁም ማንም አይወቅ” አሉት።

[20]የብራናውን ጥቅልል በጸሓፊው በኤሊሳማ ክፍል ካስቀመጡት በኋላ፣ ንጉሡ

36፥1 2ዜና36፥5
36፥2 ቍ4፤ዘፀ 17፥14፤መዝ40፥7፤ ኤር1፥2፤25፥3፤30፥2፤ ሕዝ2፥7፤ዕን2፥2
36፥3 ቍ7፤2ነገ 17፥13፤ኢሳ6፥9፤ 44፥22፤ኤር18፥8፤ 26፥3፤ሕዝ 2፥3፤ አሞ5፥15፤ማር4፥12፤ ሐሥ3፥19
36፥4 ቍ2፡18፤ኤር 32፥12፤51፥59፤ሕዝ 2፥9፤ዳን7፥1፤ዘካ5፥1
36፥6 ቍ9፤ዘፀ 4፥16፤2ዜና20፥4
36፥7 ኤር26፥3፤ 37፥20፤42፥2፤ዘዳ 31፥17
36፥9 ቍ22፤2ዜና 20፥3
36፥10 ቍ12፡25፤ ዘፍ23፥10፤ኤር26፥24 ፤29፥3፤52፥25
36፥12 2ሳሙ8፥17 ፤ኤር26፥22፤38፥4
36፥14 ቍ4፡21
36፥16 መዝ36፥1
36፥17 ኤር30፥2
36፥18 ቍ4
36፥19 1ነገ17፥3፤ ኤር26፥16

---

የተናገረውን ትንቢት የያዘውን ጽሑፍ ለማጥፋት የወሰደውን ርምጃ እንመለከታለን።

36፥1 *ኢዮአቄም በነገሠ በአራተኛው ዓመት፤* ዘመኑ በ605 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው ይህ ዘመን በይሁዳ ታሪክ ውስጥ አሥጊ ጊዜ ነበር (የ25፥1፤ 46፥2 ማብ ይመ)።

36፥2 *የብራና ጥቅልል፤* የ30፥2፤ የዘፀ17፥14 ማብ ይመ። *ጻፍበት፤* ኤርምያስ የተናገረው ትንቢት (መልእክት) ለሚመጣው ትውልድ እንዲተላለፍ ነው። *የነገርሁህን ቃል ሁሉ፤* ኤርምያስ የተናገረውን ትንቢት የያዘው የመጀመሪያው ጽሑፍ ሁሉንም ምዕራፎች ወይም ከ1-26፤ 46-51 ያሉትን አብዛኞቹን ምዕራፎች ያካተተ ሊሆን ይችላል። *ለአንተም መናገር ከጀመርሁበት ከኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት፤* የ1፥2 ማብ ይመ።

36፥3 *ምናልባትም ... እኔም፤* ሕዝቡ ንስሓ ቢገባ፣ እግዚአብሔር ይቅር ይለዋል (18፥7-10 እና ማብ እንዲሁም 26፥3 ይመ)።

36፥4 *ባሮክን፤* የ32፥12 ማብ ይመ።

36፥5 *እኔ ተከልክያለሁና፤* እንዲህ ሊሆን የቻለው በቤተ መቅደስ ለሕዝቡ በተላለፈውና ተቀባይነት ባላነበረው ትንቢቱ (7፥2-15፤ 26፥2-6 ይመ)፣ ወይም በ19፥1-20፥6 ላይ በተጻፉት ነገሮች ምክንያት ሊሆን ይችላል።

36፥6 *በጾም ቀን፤* በአገር ላይ ከመጣ ድንገተኛ ነገር የተነሣ (ከኢዮ3፥15 ጋር ያነጻጽሩ) በተለይም 605 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎን ያደረገችውን ወረራ አስመልክቶ የታወጀ የጾም ቀን ሊሆን ይችላል (ዳን1፥1 እንዲሁም ማብ ይመ)።

*36፥7፤* ቍ3 እና ማብ ይመ።

*36፥8፤* የመጽሐፉ ታሪክ ቅደም ተከተሉን የጠበቀ ቢሆን ኖሮ፣ ም45 መጻፍ የሚገባው ከዚህ ጥቅስ ቀጥሎ ነበር (በመግቢያው ሥር የተነደፈውን አስተዋጽኦ ይመ)።

36፥9 *በአምስተኛው ዓመት በዘጠነኛው ወር፤* 604 ዓ.ቅ.ክ ላይ ሲሆን፣ አየሩም ቀዝቀዝ የሚልበት ጊዜ ነበር (ቍ22 ይመ)።

*36፥10፤* ከ2ነገ23፥2 ጋር ያነጻጽሩ። *ክፍል፤* የ35፥2 ማብ ይመ። *ገማርያ፤* በለኪሶ ከተገኙት በድንጋይ ላይ ከተቀረጹት ጽሑፎች በአንዱ ላይ (የ34፥7 ማብ ይመ)፤ ከመቶ ዓመት በኋላ በኤሌፋንቲን ፓፒረስ ላይ ተጽፈው ከተገኙት መካከል ቢያንስ በሁለቱ ላይ የተጻፈ ሲሆን (የ32፥11 ማብ ይመ)፣ በኤርምያስ ዘመን የተለመደ ስም ነበር (29፥3 ይመ)። *ሳፋን፤* በንጉሥ ኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት የመንግሥቱ ዋና ጸሓፊ ነበር (2ነገ22፥3 እንዲሁም የ26፥24፤ 29፥3 ማብ ይመ)። *አዲሱ በር ... መግቢያ* 26፥10 እና ማብ ይመ።

36፥12 *የዓክቦር ልጅ ኤልናታን፤* የ26፥22 ማብ ይመ።

36፥18 *በቀለም፤* በብሉይ ኪዳን ውስጥ የተጠቀሰው እዚህ ላይ ብቻ ነው (2ቆሮ3፥3፤ 2ዮሐ ቍ12፤ 3ዮሐ ቍ13 ይመ)።

*36፥19፤* መኳንንቱም፣ የኤርምያስንና የባሮክን ደኅንነት የመጠበቁ ጕዳይ በጣም አሳስቦአቸው ነበር (ከ26፥20-23 ጋር ያነጻጽሩ)።

36፥20 *ካስቀመጡት ...፤* ጥንቃቄ ለማድረግ ተብሎ

ወዳለበት አደባባይ ሄደው የሆነውን ሁሉ
ነገሩት:: [21]ንጉሡም ብራናውን ያመጣ ዘንድ
ይሁዲን ላከው፤ ይሁዲም ከጸሓፊው ከኤሊ
ሳማ ክፍል ብራናውን አምጥቶ፣ ለንጉሡና
በንጉሡ አጠገብ ቆመው ለነበሩት መኳን
ንት ሁሉ አነበበላቸው:: [22]ዘጠነኛው ወር
እንደ መሆኑ፣ ንጉሡ የክረምትን ወራት
በሚያሳልፍበት ቤት ተቀምጦ ነበር፤ በም
ድጃ የሚነድ እሳትም ፊት ለፊቱ ነበር::
[23]ይሁዲ ከብራናው ሦስት ወይም አራት ዐምድ
ባነበበ ቍጥር ንጉሡ ብራናው ሁሉ እስከ
ሚያልቅ ድረስ በጸሓፊ ቢላዋ እየቈረጠ
እንዲቃጠል ወደ እሳቱ ምድጃ ይጥል
ነበር:: [24]ንጉሡም ሆነ ይህን ሁሉ ቃል
የሰሙት መኳንንት ሁሉ አንዳች አልፈሩም፤
ልብሳቸውንም አልቀደዱም:: [25]ኤልናታን፣
ድላያ፣ ገማርያም ንጉሡ ብራናውን እንዳያ
ቃጥል ቢለምኑትም እንኳ አልሰማቸውም፣
[26]ይልቁንም ጸሓፊውን ባሮክንና ነቢዩን
ኤርምያስን ይዘው ያስሩ ዘንድ የንጉሡን
ልጅ ይረምሕኤልን፣ የዓዝርኤልን ልጅ
ሠራያንና የአብድኤልን ልጅ ሰሌምያን
አዘዘ፤ *እግዚአብሔር* ግን ሰውሮአቸው
ነበር::

[27]ንጉሡ፣ ባሮክ ከኤርምያስ አፍ ተቀ
ብሎ የጻፈው ቃል ያለበትን ብራና ካቃጠለ
በኋላ፤ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ
እንዲህ ሲል መጣ፤ [28]"ሌላ ብራና ወስደህ፣
የይሁዳ ንጉሥ ኢዮአቄም ባቃጠለው
በመጀመሪያው ብራና ላይ የነበረውን ቃል
ሁሉ ጻፍበት፤ [29]ለይሁዳ ንጉሥ ለኢዮአቄም
እንዲህ ብለህ ንገረው፤ '*እግዚአብሔር*
እንዲህ ይላል፤ "የባቢሎን ንጉሥ በእርግጥ
ይመጣል፤ ይህቺን ምድር፣ በእርሷም ላይ
የሚኖሩትን ሰዎችንና እንስሳትን ያጠፋል

36፥21 ቍ14፡2ነገ 22፥10
36፥22 አሞ3፥15
36፥23 ቍ2፤1ነገ 22፥8
36፥24 ዘፍ37፥29፤ ዘኍ14፥6፤መዝ36፥1
36፥25 ቍ10:12
36፥26 1ነገ17፥3፤ መዝ11፥1፤ኤር1፥8፤ 15፥21፤ማቴ23፥34
36፥27 ቍ 4
36፥28 ቍ 2
36፥29 ኢሳ30፥10፤ ኤር33፥12
36፥30 2ነገ24፥6፤ ኢሳ14፥19፤ኤር8፥2፤ ኤር52፥2
36፥31 ዘዐ20፥5፤ ምሳ29፥1፤1፥24
36፥32 ቍ4:23፤ ዘዐ34፥1፤ኤር30፥2
37፥1 1ሳሙ11፥1 ፤2ነገ24፥8:12:17፤ ኤር22፥24፤ሕዝ 17፥13
37፥2 2ነገ24፥19
37፥3 ቍ17፤ዘዐ 8፥28፤ዘኍ21፥7፤ 1ሳሙ12፥19፤1ነገ 13፥6፤2ነገ19፥4፤ 25፥18፤ኤር29፥25፤ 38፥1:14፤42፥2፤ 52፥24
37፥4 ቍ15፤ኤር 32፥2
37፥5 ዘፍ 15፥18፤ ኢሳ30፥5፤31፥1፤ ኤር34፥11:21፤ሕዝ 17፥15

በማለት የጻፍህበት ለምንድን ነው?" ብለህ
ብራናውን አቃጥለሃል:: [30]ስለዚህ *እግዚ
አብሔር* ስለ ይሁዳ ንጉሥ ስለ ኢዮአቄም
እንዲህ ይላል፤ በዳዊት ዙፋን ላይ የሚቀ
መጥ ከዘሩ አይገኝም፤ ሬሳውም ወደ ውጭ
ተጥሎ ለቀን ሐሩርና ለሌት ቍር
ይጋለጣል:: [31]እርሱንና ልጆቹን መኳንንቱ
ንም ስለ ክፋታቸው እቀጣለሁ፤ አልሰ
ሙትምና አመጣባቸዋለሁ ያልሁትን ጥፋት
ሁሉ በእነርሱና በኢየሩሳሌም በሚኖሩት፣
በይሁዳም ሕዝብ ላይ አመጣለሁ::' "

[32]ኤርምያስም ሌላ ብራና ወስዶ ለኔርያ
ልጅ ለጸሓፊው ለባሮክ ሰጠው፤ ባሮክም
የይሁዳ ንጉሥ ኢዮአቄም በእሳት ባቃጠ
ለው ብራና ላይ የነበረውን ቃል ሁሉ
ከኤርምያስ አፍ ተቀብሎ ጻፈበት፤ ብዙ
ተመሳሳይ ቃልም ተጨመረበት::

## የኤርምያስ መታሰር

**37** የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር የኢ
ዮስያስን ልጅ ሴዴቅያስን በይሁዳ
ላይ አነገሠው፤ እርሱም በኢዮአቄም ልጅ
በኢኮንያን[1] ፈንታ ነገሠ:: [2]ነገር ግን እርሱም
ሆነ መኳንንቱ የምድሪቱም ሕዝብ በነቢዩ
በኤርምያስ አማካይነት የተነገረውን *የእግዚ
አብሔርን* ቃል አልሰሙም::

[3]ንጉሡ ሴዴቅያስም፣ "ወደ ስምላካችን
ወደ *እግዚአብሔር* ስለ እኛ ጸልይ" በማ
ለት የሰሌምያን ልጅ ዮካልንና ካህኑን
የመዕሤያን ልጅ ሶፎንያስን ወደ ነቢዩ ወደ
ኤርምያስ ላከ::

[4]ኤርምያስ ገና እስር ቤት ስላልገባ፣ በሕ
ዝቡ መካከል እንደ ልቡ ይወጣና ይገባ
ነበር:: [5]የፈርዖንም ሰራዊት ከግብፅ ወጥቶ
ነበርና ኢየሩሳሌምን ከበው የነበሩት ባቢ

[1] የዕብራይስጡ *ኢኮንያን የኢዮአቄም* አቻ ስም ነው::

ነው::

36፥22 ***ዘጠነኛው ወር፤*** የቍ9 ማብ ይመ:: ***የክረምትን ወራት በሚያሳልፍበት ቤት፤*** ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "የክረምት ቤት" ማለት ነው (በአሞ3፥15 ላይ እንደ ተጠቀሰው) እዚህ ላይ ግን በንጉሡ ቤተ መንግሥት ውስጥ የሚገኝ አንድ ሰፊ ክፍል ሊሆን ይችላል:: ***በምድጃ የሚነድ እሳትም፤*** ክፍሉን ለማሞቅ በክፍሉ ውስጥ መካከለኛ ቦታ ላይ የተቀመጠ የከሰል እሳት ይነድበት የነበረ ማንደጃ ነው::

*36፥23፤* ንጉሥ ኢዮስያስ የእግዚአብሔርን ቃል ለማወቅና ለመታዘዝ የነበረውን ምኞት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (2ነገ22፥11-23:3፤ 23፥21-24 ይመ):: ***ዐምድ፤*** የዐምዶቹ ቅርጽ አራት ማዕዘን ስለ ነበር፣ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "በሮች" ተብለው ይጠሩ ነበር:: ***እየቈረጠ፤*** በቀጥታ ሲተረጐም "እየቀደደ" ማለት ነው:: ንጉሡ የራሱን ልብስ በመቅደድ ፋንታ (የቍ24 ማብ ይመ) የነቢዩን ጥቅልል ብራና ቀደደ::

36፥24 ***መኳንንት ሁሉ አንዳች አልፈሩም፤*** ቍ31 ይመ:: አለቆቹ የሰጡትን መልስ (ቍ12፤ቍ16:25 ይመ) ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ:: ***ልብሳቸውንም አልቀደዱም፤*** የኢዮአቄም አባት ኢዮስያስ የሰጠውን መልስ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (2ነገ22፥11 ይመ፤ ከ1ነገ21፥27 ጋር ያነጻጽሩ)::

36፥26 ***የንጉሡን ልጅ፤*** "የንጉሥ ቤተ ሰብ" ማለት ነው (38፥6፤ 1ነገ22፥26፤ ሶፎ1፥8):: ኢዮአቄም ዕድሜው ሰላሳ ዓመት ብቻ የነበረ በመሆኑ (2ነገ23፥36)፣ ቃል በቃል በመተርጐም የሐረጉን ሐሳብ መረዳት አስቸጋሪ ሊሆን ይችላል::

36፥30 ***ኢዮአቄም ... ዙፋን ላይ የሚቀመጥ ከዘሩ አይገኝም፤*** የኢዮአቄም ልጅ ዮአኪን (2ነገ24፥2) ሦስት ወር ብቻ ገዛ (2ነገ24፥8)፤ ከዚያም በግዞት ወደ ባቢሎን ተወሰደ (2ነገ 24፥15 ይመ)፤ ቈይቶም በዚያ ሞተ (52፥33-34):: ***ሬሳውም ወደ ውጭ ተጥሎ፤*** የነቢዩን ጥቅልል ብራና እሳት ውስጥ ጥሎ (ቍ23) በማቃጠሉ (22፥18-19 እና ማብ ይመ) የደረሰበት ቅጣት ነው::

*36፥31፤* 11፥11፤ 19፥15፤ 35፥17 ይመ:: ***መኳንንቱም፤*** የቍ24 ማብ ይመ::

36፥32 ***ሌላ ብራና፤*** ከዘፀ34፥1 ጋር ያነጻጽሩ::

*37፥1-38፥28፤* በሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት የመጨረሻዎቹ ሁለቱ ዓመታት (588-586 ዓ.ቅ.ክ) ኤርምያስ በባለሥልጣኖች የታሰረባቸው ዓመታት ናቸው (20፥2 እና ማብ ይመ)::

*37፥1፤* 2ነገ24፥15:17-18 ይመ:: ***ሴዴቅያስ፤*** ትርጕሙ "እግዚአብሔር ጽድቄ ነው" ማለት ነው፤ በመግቢያው ላይ የተጻፈውን የታሪክ ዳራ ይመ:: ***በኢኮንያን ፈንታ ነገሠ፤*** ይህ የሆነው በ597 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው:: ኢዮአቄምን በተመለከተ በ36፥30 ላይ የተነገረው ትንቢት በዚህ ይፈጸማል::

37፥3 ***ሴዴቅያስም ... ኤርምያስ ላከ፤*** 21፥1 ይመ:: ***የሰሌምያን ልጅ ዮካልን፤*** ከጊዜ በኋላ ለኤርምያስ ጠላቱ ሆነ (38፥1:4 ይመ):: ***የመዕሤያን ልጅ፤ ሶፎንያስን፤*** 21፥1 እና ማብ ይመ:: ***ስለ እኛ ጸልይ፤*** 21፥2 እና ማብ ይመ፤ ምናልባት የጸሎቱ ዋና ዐላማ፣ በ588 ዓ.ቅ.ክ ላይ ባቢሎናውያን የወሰዱትን ለቆ የመውጣት ርምጃ (የ34፥21-22 ማብ ይመ) የዘለቄታ እንዲያደርገው እግዚአብሔርን መለመን ይሆናል::

37፥5 ***የፈርዖንም ሰራዊት፤*** የሖፍራ ሰራዊት (44፥30 ይመ)፣ በግሪክ ባለታሪኮች "አፕራይስ" ተብሎ ይጠራል:: ***ከግብፅ ወጥቶ፤*** ምናልባት ሴዴቅያስ በጠየቀው መሠረት እርሱን

ሎናውያን[ሠ] ይህን ሲሰሙ ኢየሩሳሌምን ለቀው ሄዱ::

[6]*የእግዚአብሔርም* ቃል ወደ ነቢዩ ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [7]"የእስራኤል ስምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ትጠይቀኝ ዘንድ ወደ እኔ የላካችሁን የይሁዳን ንጉሥ እንዲህ በሉት፤ 'ሊረዳችሁ የወጣው የፈርዖን ሰራዊት ወደ ገዛ አገሩ ወደ ግብፅ ይመለሳል፤ [8]ባቢሎናውያንም ተመልሰው ይህችን ከተማ ይወጓታል፤ ይዘውም ያቃጥሏታል::'

[9]"*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ባቢሎናውያን በእርግጥ ትተውን ይሄዳሉ' ብላችሁ አታስቡ፤ አይሄዱምና ራሳችሁን አታታሉ:: [10]የሚዋጋችሁን የባቢሎናውያንን[ረ] ሰራዊት ሁሉ አሸንፋችሁ፣ ቍስለኞች ብቻ በድንኳኖቻቸው ውስጥ ቢቀሩ እንኳ፤ እነዚህ ሰዎች መጥተው ይህችን ከተማ ያቃጥሏታል::"

[11]የባቢሎን ሰራዊት ከፈርዖን ጭፍራ የተነሣ ከኢየሩሳሌም ከወጣ በኋላ፣ [12]ኤርምያስ በሕዝቡ መካከል የርስቱን ድርሻ ለመካፈል፣ ከኢየሩሳሌም ወደ ብንያም አገር ሊሄድ ተነሣ፤ [13]ነገር ግን ወደ ብንያም በር ሲደርስ፣ የዘበኞች አለቃ የነበረው የሐናንያ ልጅ የሴሌምያ ልጅ የሪያ የተባለው፣ "ከድተህ ወደ ባቢሎናውያን ልትሄድ ነው!" በማለት ያዘው::

[14]ኤርምያስም፣ "ሐሰት ነው! ከድቼ ወደ ባቢሎናውያን መሄዴ አይደለም" አለ፤ የሪያ ግን አልሰማውም፤ እንዲያውም ኤርምያስን አስሮ ወደ መኳንንቱ አመጣው:: [15]መኳንንቱም እጅግ ተቈጥተው ኤርምያስን ደበደቡት፤ የግዞት ቤትም አድርገውት በነበረው፤ በጸሓፊው በዮናታን ቤት አሰሩት::

[16]ኤርምያስም በምድር ቤት በሚገኝ ክፍል ውስጥ እንዲቀመጥ ተደረገ፤ በዚያም ረጅም ጊዜ ቈየ:: [17]ከዚያም በኋላ ንጉሡ ሴዴቅያስ ላከበትና ወደ ቤተ መንግሥት አስመጣው፤ ለብቻውም ወስዶ፣ "*ከእግዚአብሔር* የመጣ ቃል አለህ?" በማለት ጠየቀው::

ኤርምያስም፣ "አዎን አለ፤ ለባቢሎን ንጉሥ ዐልፈህ ትሰጣለህ" አለው::

[18]ኤርምያስም ንጉሡ ሴዴቅያስን እንዲህ አለው፤ "ያሰራችሁኝ በአንተና በመኳንንትህ ወይም በዚህ ሕዝብ ላይ ምን ወንጀል ፈጽሜ ነው? [19]ለመሆኑ፣ 'የባቢሎን ንጉሥ እናንተንም ይህችንም ምድር አይወጋም' ብለው ትንቢት ይናገሩ የነበሩት ነቢያታችሁ ወዴት ናቸው? [20]አሁንም ጌታዬ ንጉሥ ሆይ፤ እባክህ አድምጠኝ፤ ልመናዬን በፊትህ ላቅርብ፤ በዚያ እንዳልሞት ወደ ጸሓፊው ወደ ዮናታን ቤት አትመልሰኝ::"

[21]ንጉሡም ሴዴቅያስ፣ ኤርምያስ በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ እንዲቀመጥና በከተማዪቱ ያለው እንጀራ እስኪያልቅ ድረስ ከእንጀራ ጋጋሪዎች ሰፈር በየቀኑ አንድ አንድ እንጀራ እንዲሰጠው አዘዘ፤ ስለዚህ ኤርምያስ በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ ተቀመጠ::

## ኤርምያስ በውሃ ጒድጓድ ውስጥ ተጣለ

**38** ኤርምያስ ለሕዝቡ የተናገረውን ቃል የማታን ልጅ ሰፋጥያስ፣ የጳስኮር ልጅ ጎዶልያስ፣ የሰሌምያ ልጅ ዮካል[ሰ] እንዲሁም የመልክያ ልጅ ጳስኮር ሰሙ፤ ቃሉም እንዲህ የሚል ነበር:- [2]"*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'በዚህች ከተማ የሚቀር ሁሉ በሰይፍ፣ በራብ ወይም በቸነፈር ይሞታል፤ ይህን ስፍራ ለቆ ወደ ባቢሎናውያን[ሸ] የሚሄድ ሁሉ ይተርፋል፤ ያመልጣል፤ በሕ

[ሠ]5 ወይም *ከለዳውያን፤* ቍ8:9:13እና 14 ይመ::
[ረ]10 ወይም *ከለዳውያን፤* ቍ11 ይመ::
[ሰ]1 የዕብራይስጡ *ዮካል የሁካል* አቻ ስም ነው::
[ሸ]2 ወይም *ከለዳውያን፤* ቍ18:19 እና23 ይመ::

37፥7 ቍ5፤ዘፍ 25፥22፤2ነገ18፥21፤ 22፥18፤ኤር2፥36፤ ሰቆ1፥7፤4፥17
37፥8 ኤር21፥10፤ 38፥3:18፤39፥8
37፥9 ኤር29፥8፤ ማር13፥5
37፥10 ኤር21፥10
37፥11 ቍ 5
37፥12 ኤር32፥9
37፥13 ኤር20፥2፤ 21፥9
37፥14 ኢሳ58፥6፤ ኤር 40፥4
37፥15 ቍ20፤1ነገ 22፥27፤ኤር20፥2፤ 38፥26፤ዕብ11፥36
37፥17 ቍ3፤ዘፍ 25፥22፤ኤር15፥11፤ 21፥7፤38፥16
37፥18 1ሳሙ 26፥18፤ዮሐ10፥32፤ ሐሥ25፥8
37፥19 ኤር14፥13 ፤ሕዝ13፥2
37፥20 ቍ 15
37፥21 ዘሌ26፥26 ፤2ነገ25፥3፤ኢሳ 33፥16፤ኤር32፥2፤ 38፥6:9:13:28፤ 39፥13-14፤ሰቆ1፥11
38፥1 ኤር37፥3፤ 1ቆሮ9፥12
38፥2 ቍ17፤ኤር 21፥9፤34፥17፤ 39፥18፤45፥5

ለመርዳት ይሆናል፤ በለኪሶ የተገኘው፣ በድንጋይ ላይ የተቀረጸው ሦስተኛ ጽሑፍ (34፥7 ማብ ይመ) የይሁዳ ሰራዊት አዛዥ ወደ ግብፅ ያደረገውን ጒብኝት ይጠቅሳል፤ ይሁን እንጂ ሴዴቅያስ በብልኀት ለማሸነፍ ያደረገው፣ እንደዚህ ያለው ሙከራ ሳይሳካ ቀረ (ሕዝ17፥15:17 ይመ):: *ባቢሎናውያን ... ለቀው ሄዱ፤* ከግብፅ ጋር ጦርነት ለመግጠም ነው (34፥21 እና ማብ ይመ)::

37፥7 *የፈርዖን ሰራዊት ... ወደ ግብፅ ይመለሳል፤* ናቡከደነፆር ሖፍራን በቀላሉ ያሸንፈዋል (የሕዝ30፥21 ማብ ይመ)::

37፥10 *ቍስለኞች፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "የተወጉ" "በጠና የቈሰሉ" ማለት ነው:: ባቢሎናውያን ከባድ መሰናከል ቢገጥማቸውም፣ አሁንም ኢየሩሳሌምን ከማጥፋት አይመለሱም::

37፥12 *ብንያም አገር፤* የኤርምያስ የተወለደባት አናቶት የምትገኘው እዚሁ ነው (የ1፥1 ማብ ይመ):: *የርስቱን ድርሻ ለመካፈል፤* 1ሳሙ30፥24 ይመ:: ባቢሎናውያን በወረሩበት ወቅት ለጥቂት ጊዜ እፎይታ ተገኝቶ ስለ ነበረ፣ ኤርምያስ ከሌሎች የቤተ ሰቡ አባላት ጋር ያለውን የርስት ጒዳይ ለማስተካከል ፈለገ::

37፥13 *ብንያም በር፤* 38፥7፤ እንዲሁም የዘካ14፥10 ማብ ይመ:: *ከድተህ ወደ ባቢሎናውያን ልትሄድ ነው፤* ኤርምያስ ለባቢሎናውያን እጅ መስጠት የሚሻል እንደ ሆነ ተናግሮ ስለ ነበርና (21፥9፤ 38፥2) ብዙ አይሁድም ከድተው ወደዚያ ስለ ገቡ (38፥19፤39፥9፤52፥15 ይመ) የሪያ የፈራበት ምክንያት ግልጽ ነው::

37፥15 *ደበደቡት፤* 20፥2 እና ማብ ይመ:: *በዮናታን ቤት፤* ኤርምያስ መለስ ብሎ ስለዚህ እስር ቤት በማሰብ ለሕይወቱ እጅግ አደገኛ ቦታ እንደ ሆነ ይናገራል (ቍ20፤ 38፥26 ይመ)::

37፥16 *በምድር ቤት፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "የውሃ ማጠራቀሚያ ቤት" ማለት ነው (ዘፀ12፥29 ይመ)::

37፥17 *ሴዴቅያስ ... ለብቻውም ... ጠየቀው፤* በሚፈራቸው ባለሥልጣኖች ፊት እንዲነግረው ስላልፈለገ ነው:: 'ለባቢሎን ንጉሥ እጅ ዐልፈህ ትሰጣለህ' አለው (32፥4፤34፥3 ይመ)::

37፥19 *ነቢያታችሁ፤* ሐሰተኞች ነቢያት ማለት ነው (ዘዳ 18፥32 ይመ)::

37፥20 *ልመናዬን በፊትህ ላቅርብ፤* 36፥7 ይመ::

37፥21 *በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ፤* በቍ16 ላይ ከተጠቀሰው ምድር ቤት ይልቅ ሻል ያለ እስር ቤት ነው (የ32፥2 ማብ ይመ):: *ከእንጀራ ጋጋሪዎች ሰፈር፤* የሚገኘው ምናልባት ከእቶኑ ግንብ አጠገብ ይሆናል (የነህ3፥11 ማብ ይመ):: ... *እንጀራ እስኪያልቅ ድረስ፤* 'ዳቦ' የሚለው የዕብራይስጥ ቃል በ52፥6 ላይ 'ምግብ' ተብሎ ተተርጒሟል::

38፥1 *የጳስኮር፤* የ20፥1 ማብ ይመ:: *የሰሌምያ ልጅ ዮካል፤* የ37፥3 ማብ ይመ:: *የመልክያ ልጅ ጳስኮር፤* የ21፥1 ማብ ይመ:: *ኤርምያስ ለሕዝቡ የተናገረውን ቃል፤* በዘብ ጠባቂዎች አደባባይ ቢታሰርም (37፥21 ይመ)፣ ጠያቂዎች እንዳይከለከሉበትና ከእነርሱም ጋር እንዲነጋገር ተፈቅዶለት ነበር (32፥8:12 ይመ)::

*38፥2፤* በ21፥9 ላይ የተጻፈውን ሐሳብ መልሶ ይጠቅሳል

ይወትም ይኖራል።' [3]*እግዚአብሔርም* እንዲህ ይላል፤ 'ይህች ከተማ በእርግጥ ለባቢሎን ንጉሥ ሰራዊት ዐልፋ ትሰጣለች፤ እርሱም ይይዛታል።' ”

[4]መኳንንቱም ንጉሡን እንዲህ አሉት፤ “ይህ ሰው በሚናገረው ነገር በዚህች ከተማ የቀሩትን ወታደሮችና ሕዝቡንም ሁሉ ተስፋ የሚያስቈርጥ ስለ ሆነ መሞት አለበት፤ ይህ ሰው የሕዝቡን መጥፋት እንጂ መልካም ነገር አይሻም።”

[5]ንጉሡ ሴዴቅያስም፤ “እርሱ በእጃችሁ ነው፤ ንጉሡ እናንተን ተቃውሞ ምንም ማድረግ አይችልም” አለ።

[6]ስለዚህ ኤርምያስን ወስደው፣ በዘበኞች አደባባይ በነበረው በንጉሡ ልጅ በመልክያ የውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓድ ውስጥ ጣሉት፤ በገመድም ኤርምያስን ወደ ጕድጓዱ አወረዱት። ጕድጓዱም ጭቃ እንጂ ውሃ አልነበረበትም፤ ኤርምያስም ወደ ጭቃው ዘልቆ ገባ።

[7]በቤተ መንግሥት ባለ ሥልጣን የነበረው ኢትዮጵያዊ[a] ጃንደረባ[b] አቤሜሌክ፣ ኤርምያስን በውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓድ ውስጥ እንደ ጣሉት ሰማ። ንጉሡም በብንያም በር ተቀምጦ ሳለ፣ [8]አቤሜሌክ ከቤተ መንግሥት ወጥቶ ንጉሡን እንዲህ አለው፤ [9]“ጌታዬ ንጉሥ ሆይ፤ እነዚህ ሰዎች በነቢዩ በኤርምያስ ላይ ባደረጉት ነገር ሁሉ ክፋትን አድርገዋል፤ ከከተማዪቱም እንጀራ በጠፋ ጊዜ በራብ እንዲሞት ጕድጓድ ውስጥ ጥለውታል።”

[10]ንጉሡም ኢትዮጵያዊውን አቤሜሌክን፣ “ሠላሳ ሰዎች ከዚህ ይዘህ ሂድ፤ ነቢዩ ኤርምያስንም ሳይሞት ከጕድጓድ አውጣው” ብሎ አዘዘው።

38፥3 ኤር21፥4፣10
38፥4 1ሳሙ17፥32፤ኤር11፥21፤36፥12
38፥5 1ሳሙ15፥24፤ኤር26፥14
38፥6 ዘፍ37፥24፤ኢሱ2፥15፤ኢዮ30፥19፤ኤር37፥21፤ሰቆ3፥53
38፥7 ኢዮ29፥7፤ኢሳ56፥3-5፤ኤር39፥16፤ሐሥ8፥27
38፥9 ዘፍ37፥20፤ኤር37፥21
38፥11 ኢሱ2፥15
38፥13 ኤር37፥21
38፥14 1ሳሙ3፥17፤ኤር37፥3
38፥16 ቍ4፤ኢሳ42፥5፤57፥16፤ኤር37፥17
38፥17 ኤር 21፥9፤27፥8
38፥18 ቍ3፤ኤር24፥8፤32፥4፤37፥8

[11]አቤሜሌክም ሰዎቹን ይዞ በቤተ መንግሥቱ ግምጃ ቤት ሥር ወዳለው ክፍል ሄደ፤ ያረጀ ጨርቅና ያለቀ ልብስ ከዚያ ወስዶ ወደ ኤርምያስ ወደ ጕድጓዱ ውስጥ በገመድ አወረደለት። [12]ኢትዮጵያዊው አቤሜሌክ ኤርምያስን፣ “ይህን ያረጀ ጨርቅና ያረጀ ልብስ ገመዱ እንዳይከረክርህ በብብትህ ሥር አድርገው” አለው፤ ኤርምያስም እንዲሁ አደረገ፤ [13]እነርሱም በገመዱ ጐትተው ከጕድጓዱ አወጡት። ኤርምያስም በዘበኞች አደባባይ ሰነበተ።

### ሴዴቅያስ ኤርምያስን እንደ ገና አነጋገረው

[14]ንጉሡ ሴዴቅያስ ወደ ነቢዩ ወደ ኤርምያስ ልኮ ወደ *እግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ሦስተኛው በር አስመጣውና፤ “አንድ ነገር እጠይቅሃለሁ፤ ምንም አትሸሽገኝ” አለው።

[15]ኤርምያስም ሴዴቅያስን፣ “መልስ ብሰጥህ አትገድለኝምን? ምክር ብሰጥህ አትሰማኝም” አለው።

[16]ንጉሥ ሴዴቅያስ፣ “ለኤርምያስ፣ እስትንፋስ የሰጠ ሕያው *እግዚአብሔርን!* በእርግጥ አልገድልህም፤ ሕይወትህንም ለሚሿት አሳልፌ አልሰጥም” ብሎ በምስጢር ማለለት።

[17]ኤርምያስም ሴዴቅያስን እንዲህ አለው፤ “የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ‘ለባቢሎን ንጉሥ የጦር መኰንኖች እጅህን ብትሰጥ፣ ሕይወትህ ትተርፋለች፤ ይህችም ከተማ አትቃጠልም፤ አንተና ቤተ ሰብህም በሕይወት ትኖራላችሁ። [18]ለባቢሎን ንጉሥ የጦር መኰንኖች እጅህን ባትሰጥ ግን ይህች ከተማ

[a]7 ከላይኛው ዐባይ አካባቢ የሚኖር ሊሆን ይችላል፤
[b]7 ወይም ሹም

(የዚያኑ ማብ ይመ)።

*38፥3፤* በ32፥28 ላይ የተጻፈውን ሐሳብ መልሶ ያስተጋባል (34፥2፤ 37፥8 ይመ)።

38፥4 *መኳንንቱም፤* በቍ1 ላይ ስማቸው ተጠቅሶአል። *ተስፋ የሚያስቈርጥ፤* ዕዝ4፥4 ይመ። ቃል በቃል ሲተረጐም “እጅ ማዛል” ማለት ሲሆን፣ በተመሳሳይ ሁኔታ በለኪሶ በተገኘው በስድስተኛው ድንጋይ ላይ የተቀረጸው ጽሑፍም (የ34፥7 ማብ ይመ)፣ “መኳንንቱ የሚናገሯቸው ቃላት ጥሩ አይደሉም፤ እጃችንን የሚያዝሉ ናቸው” የሚል ነው። ኢሳ35፥3 ያነጻጽሩ። *መልካም ነገር አይሻም፤* ይህን ሐረግ የሚገልጸው የዕብራይስጥ ቃል በ29፥7 ላይ “ሰላምንና ብልጽግናን ፈልግ” የሚል ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)። *መጥፋት ... መልካም፤* ይህን የሚገልጸው የዕብራይስጥ ቃል በኢሳ45፥7 ላይ “ብልጽግና ... ጥፋት” ተብሎ ተተርጕሞአል።

38፥5 *ንጉሡ ... ምንም ማድረግ አይችልም፤* ችሎታ ስላጣ ወይም ሥልጣን ስለሌለው ሳይሆን፣ ድፍረት በማጣቱ ነው። የገዛ መኳንንቱን ፈራቸው (ቍ25-26፤ 37፥17 እና ማብ ይመ)።

38፥6 *የውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓድ፤* ከላይ ጠበብ፣ ከታች ደግሞ ሰፋ ብሎ የተሠራ በመሆኑ ቅርጹ እንደ ቃጭል ነው (37፥16 እና ማብ ይመ)። *በንጉሡ ልጅ፤* የ36፥26 ማብ ይመ። *ጕድጓዱም ... ውሃ አልነበረበትም፤* የሴዴቅያስ መኳንንት ኤርምያስን ሊገድሉት ፈለጉ (ቍ4 ይመ) ነገር ግን ሕይወቱ በእነርሱ እጅ እንድትጠፋ አልፈለጉም ነበር (ከዘፍ37፥20-24 ጋር ያነጻጽሩ)።

38፥7 *አቤሜሌክ፤* “የንጉሥ አገልጋይ” ማለት ነው። *ንጉሡም በብንያም በር ተቀምጦ ሳለ፤* 37፥13 ይመ። እንዲሁም የዘካ14፥10 ማብ ይመ። የከተማው በር፣ ሁል ጊዜም ዳኝነት የሚታይበት፣ የከተማው ጕዳይ የሚመከርበትና የሚዘከርበት ስፍራ ነው (የዘፍ19፥1፤ የሩት 4፥1 ማብ ይመ)፣ በዚህ ጊዜ ሴዴቅያስ የተለያዩ ሕግ ነክ ጕዳዮችን በማየት ላይ ሊሆን ይችላል (2ሳሙ15፥2-4 ይመ)፤ ስለዚህም አቤሜሌክን ለመርዳት ሁኔታው አመቺ ነበር።

38፥9 *ከከተማዪቱም እንጀራ በጠፋ ጊዜ፤* 37፥21 እና ማብ ይመ።

38፥10 *ሠላሳ ሰዎች፤* የሰዎች ቍጥር በዛ ማለቱ ምናልባት መኳንንቱና ጓደኞቻቸው የኤርምያስን ሕይወት ለማዳን የሚደረገውን ሙከራ እንዳያሰናክሉ ለመከላከል ነው (ቍ4 ይመ)።

38፥11 ... *ግምጃ ቤት ሥር፤* የልብስ ማስቀመጫ መጋዘን (ቦታ) ሊሆን ይችላል (2ነገ10፥22 ይመ)።

38፥12 *ይህን ያረጀ ጨርቅና ያረጀ ልብስ ገመዱ እንዳይከረክርህ፤* አቤሜሌክ ለኤርምያስ ያሳየው ቸርነት በእግዚአብሔር ላይ መታመኑን ይገልጻል፤ እግዚአብሔርም ደግሞ መልካም አደረገለት (39፥15-18 ይመ)።

38፥13 *በዘበኞች አደባባይ ሰነበተ፤* የ32፥2 ማብ ይመ።

38፥14 *አንድ ነገር ... ምንም፤* ከእግዚአብሔር ዘንድ የሆነ ቃል ማለቱ ነው (37፥17)።

38፥16 *ሕያው እግዚአብሔርን፤* የዘፍ 42፥15 ማብ ይመ። *ሕይወትህንም ለሚሿት፤* የሴዴቅያስን መኳንንት ማለቱ ነው (ቍ4 እና ማብ ይመ)።

*38፥17-18፤* ቍ2-3፤ 21፥9-10፤ 32፥3-4፤ 34፥2-5 ይመ። *እጅህን ብትሰጥ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ ከተደበቁበት “መው

ለባቢሎናውያን ዐልፋ ትሰጣለች፤ እነርሱም ያቃጥሏታል፤ አንተም ራስህ ከእጃቸው አታመልጥም::’ ”

[19]ንጉሡም ሴዴቅያስ ኤርምያስን፣ “ወደ ባቢሎን የኰበለሉት አይሁድ እንዲያላግጡብኝ፣ ባቢሎናውያን ለእነርሱ ዐሳልፈው ይሰጡኛል ብዬ እፈራለሁ” አለው::

[20]ኤርምያስም እንዲህ አለው፤ “ዐሳልፈው አይሰጡህም፣ ብቻ የምነግርህን የእግዚአብሔር ቃል ታዘዝ፤ መልካም ይሆንልሃል፤ ሕይወትህም ትተርፋለች:: [21]እጅህን ለመስጠት እንቢ ብትል ግን፣ እግዚአብሔር የገለጠልኝ ነገር ይህ ነው፤ [22]በይሁዳ ቤተ መንግሥት የቀሩ ሴቶች ሁሉ ወደ ባቢሎናውያን ባለ ሥልጣኖች ይወሰዳሉ፤ ሴቶቹም እንዲህ ይላሉ፤

“ ‘እነዚያ የተማመንህባቸው ወዳጆችህ፣
አሳሳቱህ፤ አሸነፉህ::
እግርህ ጭቃ ውስጥ ተሰንቅሮአል፣
ወዳጆችህ ጥለውህ ሄደዋል::’

[23]“ሚስቶችህና ልጆችህ ሁሉ ተወስደው ለባቢሎናውያን ይሰጣሉ፤ አንተም ራስህ በባቢሎን ንጉሥ ትያዛለህ እንጂ ከእጃቸው አታመልጥም፤ ይህችም ከተማ በእሳት ትቃጠላለች::”[+]

[24]ሴዴቅያስም ኤርምያስን እንዲህ አለው፤ “ስለዚህ ስለ ተነጋገርነው ነገር ማንም አይወቅ፤ አለዚያ ትሞታለህ:: [25]መኳንንቱ ከአንተ ጋር እንደ ተነጋገርሁ ሰምተው ወደ አንተ ቢመጡና፣ ‘ንጉሡን ምን እንዳልኸው፣ ንጉሡም ምን እንዳለህ ንገረን፤ ሳትደብቅ ንገረን፤ አለዚያ እንገድልሃለን’ ቢሉህ፣ [26]‘በዚያ እንዳልሞት ወደ ዮናታን ቤት አትመልሰኝ ብዬ ንጉሡን ስለምን ነበር’ በላቸው::”

[27]መኳንንቱ ሁሉ ወደ ኤርምያስ መጥተው ጠየቁት፤ እርሱም ንጉሡ ያዘዘውን ቃል ሁሉ ነገራቸው፤ ከንጉሡ ጋር የተነጋገሩትን ነገር የሰማ አንድም ሰው ስላልነበረ፣ ከዚህ በላይ አላነጋገሩትም::

[28]ኢየሩሳሌም እስከ ተያዘችበት ቀን ድረስ ኤርምያስ በዘበኞች አደባባይ ተቀመጠ::

38፥19 ኢሳ 51፥12፤ኤር39፥9፤52፥15፤ዮሐ12፥42
38፥20 ዘዳ5፥33፤ኢሳ55፥3፤ኤር11፥4፤40፥9
38፥22 ኢዮ19፥14፤30፥19፤መዝ69፥14፤ኤር 6፥12፤13፥21
38፥23 2ነገ25፥6፤ኤር24፥8፤21፥10፤32፥4፤37፥8፤ሕዝ17፥15
38፥24 ኤር37፥17
38፥26 1ሳሙ16፥2፤ኤር37፥15
38፥28 ኤር37፥21
39፥1 2ነገ24፥1፤25፥1፤2ዜና36፥11፤ኤር25፥29፤28፥14፤52፥4፤ሕዝ4፥3፤24፥2
39፥2 2ነገ14፥13፤ሕዝ33፥21፤ዘካ8፥19
39፥3 ቍ13፤ኤር21፥4
39፥4 ኢሳ22፥11፤ሕዝ12፥12
39፥5 ዘኍ34፥11፤ኤር21፥7፤24፥8፤32፥4

### የኢየሩሳሌም መውደቅ

39፥1-10 ተጓ ምብ-2ነገ25፥1-12፤ኤር52፥4-16

**39** ኢየሩሳሌም የተያዘችው እንዲህ ነበር፤ በይሁዳ ንጉሥ በሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት በዘጠነኛው ዓመት በዐሥረኛው ወር፣ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ሰራዊቱን ሁሉ አሰልፎ በመምጣት ኢየሩሳሌምን ከበባት:: [2]በሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት በዐሥራ አንደኛው ዓመት በአራተኛው ወር፣ በወሩም በዘጠነኛው ቀን የከተማዪቱ ቅጥር ተሰበረ:: [3]የባቢሎን ንጉሥ መኳንንት ሁሉ:- የሳምጋሩ ኤርጌል ሳራስር፣ ዋና አዛዡ ናቦሠርሰኪም[*]፣ ከፍተኛው ሹም ኤርጌል ሳራሳር እንዲሁም ሌሎቹ የባቢሎን ንጉሥ መኳንንት ሁሉ ገብተው በመካከለኛው በር ተቀመጡ:: [4]የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስና ወታደሮቹ ሁሉ እነርሱን ባዩ ጊዜ ሸሹ፤ በሌሊት በንጉሡ አትክልት ስፍራ በኩል አድርገው በሁለቱ ቅጥር መካከል ከከተማዪቱ ወጡ፤ ወደ ዓረባም[¬] አመሩ::

[5]የባቢሎን[’] ሰራዊት ግን ተከትሎ አሳደዳቸው፣ በኢያሪኮም ሜዳ ደርሶባቸው ሴዴቅያስን ያዘ፤ ማርከውም በሐማት ምድር

[+]23 ወይም *ይህችም ከተማ በእሳት እንድትቃጠል ምክንያት ትሆናለችሁ*
[*]3 ወይም *ኤርጌል ሳርስር፣ ሳምጋር ናባ፣ ሠርሰኪም*
[¬]4 ወይም *በዮርዳኖስ ሸለቆ* [’]5 ወይም *ከለዳውያን*

ጣት” ማለት ነው (2ነገ18፥31፤ 24፥12 ይመ):: *ለባቢሎን ንጉሥ የጦር መኰንኖች፤* በኢየሩሳሌም ላይ የተደረገውን ከበባ በኀላፊነት የሚመሩ ሰዎች ናቸው (39፥3:13)::

38፥19 *እፈራለሁ፤* ቍ5 እና ማብ ይመ:: ሴዴቅያስ በእግዚአብሔር ቢታመን ኖሮ አለቆችንም ሆነ ከድተው ወደ ባቢሎናውያን የገቡትን ባልፈራም ነበር (ምሳ29፥25 ይመ):: *ወደ ባቢሎን የኰበለሉት፤* 37፥13 እና ማብ ይመ:: *እንዲያላግጡብኝ፤* መሳ19፥25፤ 1ዜና10፥4 ይመ::

38፥22 *ቤተ መንግሥት ... ሴቶች ... ባለ ሥልጣኖች ይወሰዳሉ፤* ድል በሆነው ንጉሥ ቤት የነበሩትን ሴቶች አሸናፊዎቹ የራሳቸው ያደርጓቸው ነበር (ከ2ሳሙ 16፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ):: *እነዚያ የተማመንህባቸው ወዳጆችህ አሳሳቱህ፤ አሸነፉህ፤* ይህ ሐሳብ በትንቢተ አብድዩ ቍ7 ላይ ቃል በቃል ተደጋግሞአል (20፥10 እና ማብ ይመ):: የሴዴቅያስ ወዳጆች (ጓደኞች) የተባሉት የገዛ ባለ ሥልጣኖቹና (ቍ4 ይመ) ሐሰተኞች ነቢያት ነበሩ (37፥19 ይመ):: *እግርህ ጭቃ ውስጥ ተሰንቅሮአል፤* ተስፋ የመቍረጥ ምሳሌ ነው (መዝ69፥14)::

38፥26፤ 37፥20 ይመ:: *ዮናታን ቤት፤* 37፥15 እና ማብ ይመ::

38፥27 *እርሱም ንጉሡ ያዘዘውን ቃል ሁሉ ነገራቸው፤* ኤርምያስ፣ ከዚህ ውጭ ከንጉሡ ጋር በምስጢር የተነጋገሩትን ለመኳንንቱ እንዲናገር አልተገደደም::

38፥28 *በዘበኞች አደባባይ ተቀመጠ፤* ቍ13፤ እንደዚሁም የ32፥2 ማብ ይመ::

*39፥1-45፥51* ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምን ድል ማድረጋቸውንና ያስከተለውን ውጤት በሚመለከትም ከየትኛውም የብሉይ ኪዳን ክፍል ይልቅ ሰፋ ባለ ሁኔታ ይገልጻል:: አጠር ባለ ተጨማሪ ሐሳብም ይደመድማል (ም45)::

*39፥1-10፤* ስለ ኢየሩሳሌም መከበብ፣ መውደቅና ነዋሪዎቿ በምርኮ ስለ መሄዳቸው የሚገልጽ አጭር የማጠቃለያ ሐሳብ ነው (52፥4-27 ይመ)::

*39፥1-2፤* በ52፥4-7 ላይ ያለውን ዋና ሐሳብ ያቀርባል::

39፥1 *በሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት፣ በዘጠነኛው ዓመት በዐሥረኛው ወር፤* ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምን በመጨረሻ የከበቧት በወሩ በዐሥረኛው ቀን (52፥4፤2ነገ25፥1 ሕዝ24፥1-2 ይመ) ወይም የካቲት15 588 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው::

39፥2 *በዐሥራ አንደኛው ዓመት በአራተኛው ወር በወሩም በዘጠነኛው ቀን፤* ሐምሌ15 586 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው (52፥5-6፤ 2ነገ 25፥2-3 ይመ):: ከበባው ከሁለት ዓመት ተኩል በላይ ቈይቶአል::

39፥3 *በመካከለኛው በር ተቀመጡ፤* በ1፥15 ላይ የተጻፈው ሐሳብ ይፈጸም ዘንድ ነው:: መካከለኛው በር የሚገኘው፣ ምናልባት በጽዮን ተራራ ላይ ያለውን ምሽግ ከታችኛው ከተማ በሚለየው ግምብ ውስጥ ሊሆን ይችላል፤ ይህም ወራሪዎችን ለመከላከል ምቹና ጠቃሚ ቦታ ነበር:: *ኤርጌል ሳራስር፤* “ኤርጌል (የጣዖት አምላክ፤ 2ነገ17፥30 ይመ) ንጉሡን ጠብቅ” ማለት ነው:: እዚህ ላይ ስማቸው ከተጠቀሰው ሁለት ሰዎች (ቍ13 ይመ) አንዱ ምናልባት ኤርጌልሳር ይሆናል፤ እርሱም በኋላ በናቡከደነፆር ፋንታ የባቢሎን ገዥ (መሪ) ሆኖአል (560-556ዓ.ቅ.ክ):: *ከፍተኛው ሹም፤* ቍ13፤ እንዲሁም የ2ነገ18፥17 ማብ ይመ:: *መኳንንት፤* ቍ13 ይመ::

*39፥4-7፤* 52፥7-11፤ 2ነገ25፥4-7 እና ማብ ይመ::

39፥5 *ሜዳ፤* ይህ ቃል በዕብራይስጥ “ዓረባ” የሚለው ቃል ብዙ ቍጥር ነው (ቍ4)::

ወዳለችው ወደ ሪብላ ወደ ባቢሎን ንጉሥ ወደ ናቡከደነፆር አመጡት፤ በዚያም ፍርድ ወሰነበት። [6]የባቢሎንም ንጉሥ በሪብላ የሴዴቅያስን ወንዶች ልጆች፣ አባታቸው እያየ ዐረዳቸው፤ የይሁዳን መሳፍንት ሁሉ ገደላቸው፤ [7]የሴዴቅያስንም ዐይኖች አወጣ፤ ወደ ባቢሎን ሊወስደውም በናስ ሰንሰለት አሰረው።

[8]ባቢሎናውያን[ፐ] ቤተ መንግሥቱንና የሕዝቡን ቤት በእሳት አቃጠሉ፤ የኢየሩሳሌምንም ቅጥር አፈረሱ። [9]የባቢሎን መንግሥት የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡዘረዳን፣ በከተማይቱ የቀረውን ሕዝብ ሁሉ ማርኮ ወደ ባቢሎን ወሰዳቸው። [10]ንብረት ያልነበራቸውን ድኾች ግን የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡዘረዳን፣ በይሁዳ ምድር ተዋቸው፤ በዚያ ጊዜም የወይን አትክልት ቦታና የዕርሻ መሬት ሰጣቸው።

[11]የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በክብር ዘበኞቹ አዛዥ በናቡዘረዳን በኩል ስለ ኤርምያስ እንዲህ የሚል ትእዛዝ ሰጠ፤ [12]"ውሰደውና እንክብካቤ አድርግለት፤ የሚፈልገውን ነገር ፈጽምለት እንጂ አትጒዳው።" [13]የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡዘረዳን፣ ዋና አዛዡ ናቡሽዝባን፣ ከፍተኛ ሹሙ ኤርጌል ሳራስር እንዲሁም ሌሎች የባቢሎን ንጉሥ መኳንንት ሁሉ፣ [14]ልከው ኤርምያስን ከዘበኞች አደባባይ አስወጡት፤ የሳፋን ልጅ የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስ ወደ ቤቱ እንዲወስደው በዐደራ ሰጡት፤ ኤርምያስም በራሱ ሕዝብ መካከል ተቀመጠ። [15]ኤርምያስ በዘበኞች አደባባይ ታስሮ በነበረበት ጊዜ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ እርሱ እንዲህ ሲል መጣ፤ [16]"ሂድና ለኢትዮጵያዊው አቤሜሌክ እንዲህ በለው፤ 'የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ እድገት ሳይሆን ጥፋት በማምጣት በዚህች ከተማ ላይ ቃሌን እፈጽማለሁ፤ በዚያ ጊዜ በዐይንህ እያየህ ይህ ይፈጸማል። [17]አንተን ግን በዚያን ቀን አድንሃለሁ፤' ይላል *እግዚአብሔር*፤ ለምትፈራቸው ሰዎች ዐልፈህ አትሰጥም። [18]እታደግሃለሁ፤ በእኔ ታምነሃልና በሕይወት ታመልጣለህ እንጂ በሰይፍ አትወድቅም፤ ይላል *እግዚአብሔር*።'"

## ኤርምያስ በነጻነት መኖሩ

**40** የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡዘረዳን ኤርምያስን ከኢየሩሳሌምና ከይሁዳ ወደ ባቢሎን በሚወሰዱት ምርኮኞች ሁሉ መካከል በራማ በሰንሰለት ታስሮ ባገኘው ጊዜ አስፈታው፤ ከዚህ በኋላ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ መጣ። [2]የዘበኞቹ አዛዥ ኤርምያስን ለብቻው ወስዶ፣ እንዲህ አለው፤ "አምላክህ *እግዚአብሔር* በዚህች ምድር ላይ ይህን ጥፋት ተናገረ፤ [3]አሁንም *እግዚአብሔር* አመጣው፤ እንደ ተናገረውም አደረገ። ይህ ሁሉ የሆነው እናንተ *በእግዚአብሔር* ላይ ኀጢአት ስለ ሠራችሁና እርሱን ስላልታዘዛችሁ ነው። [4]እነሆ፤ ዛሬ የእጅህን ሰንሰለት ፈታሁልህ። ከፈለግህ ከእኔ ጋር ወደ ባቢሎንና፤ እኔም እንከባከብሃለሁ፤ ካልፈለግህ ግን አትምጣ። እነሆ፣ አገሪቱ ሁሉ በፊትህ ናት፤ ደስ ወዳሰኘህ ሂድ።" [5]ኤርምያስ ገና መልስ ሳይሰጥ[ኣ] ናቡዘረዳን በመቀጠል፣ "የባቢሎን ንጉሥ በይሁዳ ከተሞች ላይ ወደ ሾመው ወደ ሳፋን ልጅ ወደ አኪቃም ልጅ ወደ ጎዶልያስ ተመለስ፤ ከእርሱም ጋር በሕዝቡ መካከል ተቀመጥ፤ ወይም ደስ ወዳሰኘህ ስፍራ ሂድ" አለው። የዘበኞቹ አዛዥ ስንቅና ስጦታ ሰጥቶ አሰናበተው፤ [6]ኤርምያስም የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስ ወዳለበት ወደ ምጽጳ ሄደ፤ ከእርሱም ጋር በምድሪቱ በቀረው ሕዝብ መካከል ኖረ።

[ፐ]8 *ወይም ከለዳውያን*
[ኣ]5 *ወይም ኤርምያስ ሳይመልስ*

39፥6 ኢሳ34፥12
39፥7 ዘኍ16፥14፤ ኤር2፥35፤ሕዝ12፥13
39፥8 ነህ1፥3፤መዝ 80፥12፤ኢሳ22፥5፤ ኤር34፥22፤ሰቈ2፥8
39፥9 ኤር21፥9፤ 40፥1፤ሰቈ1፥5
39፥12 ምሳ16፥7፤ ኤር15፥20-21፤ 1ጴጥ 3፥13
39፥13 ቍ 3
39፥14 2ነገ25፥22 ፤22፥3፤12፤ነህ3፥25፤ ኤር37፥21፤40፥5
39፥16 ኢሱ23፥15፤ መዝ33፥11፤ኢሳ 14፥27፤40፥8፤ኤር 21፥10፤38፥7፤44፥28 ፤ሰቈ2፥17፤ማቴ1፥22
39፥17 መዝ34፥22 ፤41፥1-2
39፥18 1ሳሙ 17፥47፤ኢዮ5፥20፤ ኤር17፥7፤21፥9፤ 38፥2፤ሐሥ16፥31፤ ሮሜ10፥11
40፥1 ዘዳ21፥10፤ ኢሱ18፥25፤1ሳሙ 8፥4፤2ነገ24፥1፤2ዜና 36፥10፤ናሆ3፥10፤ ማቴ2፥18
40፥2 ኢሱ23፥15፤ 2ዜና34፥24፤መዝ 18፥18፤ምሳ8፥36፤ ኢሳ10፥22፤ሮሜ 13፥4፤ገላ6፥7-8
40፥3 ዘሌ26፥33፤ ዘዳ28፥45-52፤29፥ 24-28፤31፥17-18፤ 1ነገ9፥9፤ምሳ13፥21፤ ኤር22፥8-9፤ዳን 9፥14፤ሐሥ7፥39፤ ሮሜ2፥5-9፤6፥23፤ ያዕ1፥15
40፥4 ዘፍ13፥9፤ መዝ105፥18-20፤ ኤር37፥14፤ሰቈ3፥7
40፥5 ዘፍ32፥20፤ 1ሳሙ9፥7፤2ነገ 22፥12-14፤25፥22፤ ነህ5፥14፤ኤር39፥14፤

*39፥8-10፤* 52፥12-16፤ እንዲሁም 2ነገ25፥8-12 እና ማብ ይመ።

39፥12 *እንክብካቤ አድርግለት፤* የ40፥4 ማብ ይመ።

39፥13 *ኤርጌል ሳራሰር፤* የቍ3 ማብ ይመ።

39፥14 *ኤርምያስን ... አስወጡት፤* ይህም፣ 1)ኤርምያስ ከእስር ቤት መውጣቱን ባጭሩ ይገልጻል፤ የዚህ ዝርዝር ታሪክ ግን በ40፥1 ላይ በግልጽ ተቀምጦአል፤ 2)ከእስር ቤት ከወጣባቸው ሁለት ጊዜዎች ውስጥ የመጀመሪያውን በአጭሩ የሚገልጽ ይሆናል፤ እንደ ገና ከእስር ስለ መፈታቱ በ40፥1-6 ላይ በግልጽ ተጽፎአል። *ከዘበኞች አደባባይ፤* የ32፥2 ማብ ይመ። *የሳፋን ልጅ የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስ፤* የ26፥24 ማብ ይመ። *ወደ ቤቱ፤* ወደ ግዥው መኖሪያ ቤት ማለት ነው።

*39፥15-18፤* የ38፥12 ማብ ይመ።

39፥16 *ሂድና ... በለው፤* ኤርምያስ በእስር ላይ ቢሆንም እንኳ፣ ጠያቂ አልተከለከለበትም ነበር (የ38፥1 ማብ ይመ)። *በዚህች ከተማ ላይ ቃሌን እፈጽማለሁ፤* 19፥15 ይመ።

39፥17 *ለምትፈራቸው ሰዎች፤* በአቤሜሌክ አስተሳሰብ፣ "ክፉ አድርገዋል" (38፥9) ያላቸው ሰዎች የቤተ መንግሥቱ ሹማምንት ነበሩ (38፥1 ይመ)።

39፥18 *በሕይወት ታመልጣለህ፤* የ21፥9 ማብ ይመ። *በእኔ ታምነሃልና፤* አቤሜሌክ፣ ኤርምያስን ከጒድጓድ እንዲወጣ በማድረግ፣ በእግዚአብሔር ላይ ያለውን እምነት ገልጾ ነበር (38፥7-13፤ እንዲሁም የ38፥12 ማብ ይመ)።

*40፥1-44፥30፤* የኢየሩሳሌም መውደቅ ያስከተለውን ውጤት የሚገልጽ ትረካ ነው። በታሪኩ ቅደም ተከተል መሠረት፣ እነዚህ ምዕራፎች የመጽሐፉ መጨረሻ ክፍል ናቸው፤ 52፥31-34 የመጨረሻው ምዕራፍ ቢሆንም፣ ተጨማሪ ሆኖ የገባ እንጂ ከዋናው የመጽሐፉ ክፍል የሚመደብ አይደለም።

40፥1 *ቃል ... መጣ፤* በ1፥2 ላይ የተጠቀሰው "ቃል ... መጣ" የሚለው ሐረግ ኤርምያስ ከተጠራበት ጊዜ አንሥቶ በምርኮ እስከ ሄደበት ድረስ የተናገረውን ትንቢት እንደሚያሳውቅ ሁሉ፣ ይህም ከምርኮ በኋላ ኤርምያስ የተናገረውን ትንቢት የሚገልጽ ርእስ ነው። *ናቡዘረዳን ... አስፈታው፤* የ39፥14 ማብ ይመ። *ራማ፤* የ31፥15 ማብ ይመ። *ሰንሰለት፤* ከብረት የተሠራ የእጅ ማሰሪያ ነገር ነው (ቍ4፤ እንዲሁም የኢዮ36፥8፤ የኢሳ 45፥14 ማብ ይመ)።

*40፥2-3፤* ናቡዘረዳን፣ ኤርምያስ በኢየሩሳሌም ላይ የተናገረው የትንቢቱ ቃል ይዘት ምን እንደ ሆነ ያለ አንዳች ጥርጥር ዐውቆአል፤ እዚህም ላይ ዋናውን ሐሳብ ባጭሩ ለራሱ ለነቢዩ ይነግረዋል።

40፥4 *እንከባከብሃለሁ፤* ናቡዘረዳን፣ ናቡከደነፆር ለኤርምያስ ያሰበውን መልካም ነገር እንዲፈጽምለት ቃል ይገባል (39፥12 ይመ)። *አገሪቱ ሁሉ በፊትህ ናት፤* በዘፍ13፥9 ላይ አብርሃም ለሎጥ ካቀረበው ምርጫ ጋር ያነጻጽሩ።

*40፥5-9፤* 2ነገ25፥22-24 እና ማብ ይመ።

40፥5 *አኪቃም ልጅ ... ጎዶልያስ፤* የ26፥24 ማብ ይመ። *ስንቅና፤* በዕብራይስጥ በ52፥34 ላይ "ቀለብ" ተብሉአል።

## የጎዶልያስ መገደል

40፥7-9፤ 41፥1-3 ተጓ ምብ-2ነገ25፥22-26

[7]በየሜዳው የነበሩት የጦር መኰንኖችና ሰዎቻቸው ሁሉ የባቢሎን ንጉሥ የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስን በምድሪቱ ላይ ገዥ አድርጎ እንደ ሾመውና ወደ ባቢሎን በምርኮ ባልተወሰዱት በምድሪቱ ድኾች ወንዶች፣ ሴቶችና ልጆች ላይ ሥልጣን እንደ ሰጠው በሰሙ ጊዜ፣ [8]ወደ ምጽጳ፣ ጎዶልያስ ዘንድ መጡ፤ የናታንያ ልጅ እስማኤል፣ የቃሬያ ልጆች ዮሐናንና ዮናታን፣ የተንሑት ልጅ ሠራያ፤ የነጦፋዊው የዮፌ ልጆች፣ የማዕካታዊ ልጅ ያእዛንያን[ሀ] ሰዎቻቸውም ነበሩ:: [9]የሳፋን ልጅ የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስ ለእነርሱና ለሰዎቻቸው እንዲህ ሲል ቃል ገባላቸው፤ “ለባቢሎናውያን[ለ] መገዛት አትፍሩ፤ በምድሪቱ ተቀምጣችሁ የባቢሎንን ንጉሥ አገልግሉ፤ መልካም ይሆንላችኋል:: [10]እኔም ራሴ ወደ እኛ በሚመጡት በባቢሎናውያን ፊት ልቆምላችሁ፣ በምጽጳ እቀመጣለሁ፤ እናንተ ግን ወይን፣ የበጋ ፍሬና ዘይት አምርቱ፤ በማከማቻ ዕቃዎቻችሁ ውስጥ ክተቱ፤ በያዛችኋቸውም ከተሞች ተቀመጡ::”

[11]በሞዓብ፣ በአሞን፣ በኤዶምና በሌሎች አገሮች ሁሉ የነበሩ አይሁድ በሙሉ የባቢሎን ንጉሥ፣ ሰዎችን በይሁዳ እንዳስቀረና የሳፋን ልጅ የአኪቃምን ልጅ ጎዶልያስን በላያቸው እንደ ሾመ በሰሙ ጊዜ፣ [12]ሁላቸውም ከተበታተኑበት አገር ሁሉ ወደ ይሁዳ ምድር ተመለሱ፤ በምጽጳ ወደሚኖረውም ወደ ጎዶልያስ መጡ፤ ወይንና የበጋ ፍሬም በብዛት አከማቹ:: [13]የቃሬያ ልጅ ዮሐናንና ገና በየሜዳው የነበሩት የጦር መኰንኖች ሁሉ ወደ ጎዶልያስ ወደ ምጽጳ መጥተው፣ [14]“የአሞናውያን ንጉሥ በአሊስ አንተን ለመግደል የናታንያን ልጅ እስማኤልን እንደ ላከው አታውቅምን?” አሉት:: የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስ ግን አላመናቸውም::

[15]የቃሬያ ልጅ ዮሐናን፣ “ማንም ሳያውቅ የናታንያን ልጅ እስማኤልን ሄጄ ልግደለው፤ ሸሽተው ወደ አንተ የመጡት አይሁድ እንዲበተኑ፣ በይሁዳም የቀሩት እንዲጠፉ ለምን ይገድልሃል?” ብሎ በምጽጳ ለጎዶልያስ በምስጢር ነገረው::

[16]የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስ ግን የቃሬያን ልጅ ዮሐናንን፣ “ስለ እስማኤል የምትነግረኝ ሁሉ እውነት አይደለምና ይህን ነገር አታድርግ” አለው::

**41** ከንጉሣዊ ቤተ ሰብ የሆነው ከንጉሡ የጦር መኰንንኖች አንዱ የነበረው የኤሊሳማ ልጅ የናታንያ ልጅ እስማኤል፣ በሰባተኛው ወር ከዐሥር ሰዎች ጋር ወደ ምጽጳ ወደ አኪቃም ልጅ ወደ ጎዶልያስ መጣ፣ በዚያም በአንድነት ሊበሉ በማእድ ተቀምጠው ሳለ፣ [2]የናታንያ ልጅ እስማኤልና አብረውት የነበሩ ዐሥሩ ሰዎች ተነሥተው፣ የባቢሎን ንጉሥ በምድሪቱ ላይ ገዥ አድርጎ የሾመውን የሳፋንን ልጅ የአኪቃምን ልጅ ጎዶልያስን በሰይፍ መቱት፤ ገደሉትም:: [3]ደግሞም እስማኤል በምጽጳ ከጎዶልያስ ጋር የነበሩትን አይሁድ ሁሉ፣ በዚያም የተገኙትን የባቢሎን[ሐ] ወታደሮች ገደላቸው::

[4]ጎዶልያስ በተገደለ ማግስት፣ ማንም ስለ ሁኔታው ከማወቁ በፊት፣ [5]ሰማንያ ሰዎች ጢማቸውን ተላጭተው፣ ልብሳቸውን ቀደው፣ ገላቸውን ነጭተው የእህል ቍርባንና ዕጣን በመያዝ ከሴኬም፣ ከሴሎና ከሰማርያ ወደ እግዚአብሔር ቤት ለማቅረብ መጡ:: [6]የናታንያ ልጅ እስማኤል ሊገናኛቸው እያለቀሰ ከምጽጳ ወጣ፣ ሲያገኛቸውም፣ “ወደ አኪቃም ልጅ ወደ ጎዶልያስ ኑ” አላቸው:: [7]ወደ ከተማዪቱ በገቡ ጊዜ፣ የናታንያ ልጅ እስማኤልና አብረውት የነበሩ ሰዎች ዐረዷቸው፤ በውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓድ ውስጥም ጣሏቸው:: [8]ከተገደሉት

[ሀ]8 የዕብራይስጡ *ያእዛንያን የያዛንያ* አቻ ስም ነው

[ለ]9 ወይም *ከለዳያን*፤ ቍ10 ይመ

[ሐ]3 ወይም *የከለዳውያን*

41፥2፤44፥2፤ዘካ1፥12
40፥6 ቍ10፤መሳ 20፥1፤1ሳሙ7፥5-17
40፥7 ዘፍ41፥41፤ 2ነገ24፥14፤ነህ5፥14፤ ሐሥ24፥17፤ያዕ2፥5
40፥8 ቍ13፡14፡15 ፤ዘዳ3፥14፤2ሳሙ23፥ 28፤ኤር41፥1፡2፡11
40፥9 ኤር5፥19፤ 27፥11፤38፥20፤ሰቆ 1፥1፤ሕዝ23፥23፤ሮሜ 13፥1-2፤ኤፌ6፥5-8
40፥10 ቍ6፤ዘፍ 27፥28፤ዘፀ7፥19፤ 23፥16፤ ዘዳ1፥39፤ 2ቆሮ4፥7
40፥11 ዘፍ25፥30፤ ዘኍ21፥11፤25፥1፤ ኤር12፥14
40፥12 ኤር43፥5
40፥13 ቍ8፤ኤር 42፥1
40፥14 ቍ8፤ዘፍ 19፥38፤2ሳሙ10፥1-19፤ኤር25፥21፤ 41፥10፤49፥1
40፥15 ቍ8፤ዘፍ 11፥4፤ዘሌ26፥33፤ ዘዳ5፥17፤2ነገ21፥14 ፤ኢሳ1፥9፤ማቴ5፥21-22፤26፥31፤ዮሐ11፥5 2፤ሮሜ11፥5፤ያዕ1፥1
40፥16 ኤር 43፥2
41፥1 ኤር 40፥8
41፥2 ኢሱ11፥10፤ 2ሳሙ3፥27፤20፥9-10 ፤መዝ41፥9፤109፥5፤ ኤር40፥5፡8፡15፤ዕብ 11፥37
41፥5 ዘፍ12፥6፤ 33፥18፤37፥29፤ዘሌ 10፥6፤19፥27፡28፤ ዘኍ16፥40፤ኢሱ 18፥1፤መሳ9፥1-57፤ 1ነገ3፥2፤6፥38፤ 12፥1፤16፥24፤2ነገ 25፥9፤ኤር47፥5፤ 48፥37፤ማር14፥63፤ ሉቃ1፥9
41፥6 2ሳሙ3፥16፤ መዝ5፥9፤ሆሴ7፥11፤ ራእ20፥10
41፥7 ዘፍ37፥24፤ 2ነገ10፥14

40፥10 *የበጋ ፍሬና ዘይት አምርቱ፤* ናቡዘረዳን ኢየሩሳሌም የደረሰው (39፥9 ይመ) በነሐሴ 586 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነበር (የ52፥12 ማብ ይመ):: በመካከለኛው ምሥራቅ በነሐሴና በመስከረም ወር ወይን፣ የበለስ ፍሬና ዘይት የሚደርስበት ወቅት ነው::

40፥14 *በአሊስ፤* 1)ስድስት መቶ ዓ.ቅ.ክ ላይ በዮርዳኖስ አካባቢ ተቈፍሮ በተገኘው ጠርሙስ ላይ ስሙ ተጽፎ የተገኘው “ንጉሥ ባሌይ” ወይም 2)በዮርዳኖስ ውስጥ በ1984 ዓ.ም ቤቴል ኤል ኡሜሪ በተገኘው ማኅተም ላይ ስሙ የተጻፈው አሞናዊ ንጉሥ በኣል የሻ ሊሆን ይችላል:: *አሞናውያን፤* አሞን፣ ባቢሎንን ለመውጋት ቀደም ሲል ኅብረት ከፈጠሩት አገሮች አንዷ ናት (27፥3 እና ማብ፤ እንደዚሁም ሕዝ21፥18-32 ይመ)::

40፥15 *የቀሩት፤* የ6፥9 ይመ:: *በምሥጢር፤* የ38፥16 ማብ ይመ::

40፥16 *እውነት አይደለም፤* ቀጥተኛ ትርጕሙ “ውሸት” ማለት ነው (37፥14 እና ማብ ይመ):: ጐዶልያስ ስለ እስማኤል ጨዋነት የነበረው ንጹሕ እምነት ሕይወቱን እንዲያጣ አደረገው::

*41፥1-3፤* 2ነገ25፥25 እና ማብ ይመ::

41፥1 *ከንጉሡ የጦር መኰንኖች አንዱ፤* እስማኤል፣ የባቢሎን መንግሥት አሻንጉሊት መንግሥት ሆኖ የተቀመጠውን ጎዶልያስን መግደሉ፣ ለሴዴቅያስ የነበረውን ታማኝነት ይገልጻል:: *በአንድነት ሊበሉ በማዕድ ተቀምጠው ሳለ፤* እንግዳ ከመቀበል አንጻር እንዲህ ማድረጉ ጥንታዊ ባህል ስለ ነበር መገደል ቀርቶ እንግዶቹ ይጐዱኛል የሚል ግምት እንኳ ጎዶልያስ አልነበረውም (የመሳ4፥21 ማብ ይመ)::

41፥5 *ጢማቸውን ተላጭተው፣ ልብሳቸውን ቀደው፣ ገላቸውን ነጭተው፤* ምናልባት ኢየሩሳሌም በመጥፋቷ የተደረገ የሐዘን ምልክት ሊሆን ይችላል (16፥6 እና ማብ እንዲሁም የዕዝ 9፥3 ማብ፤ ይመ):: *መጡ፤* የመጡት የዳስ በዓልን ለማክበር (የዘፀ23፥16 ማብ ይመ) በሰባተኛው ወር ነው (ቍ1):: *ሴኬም፣ ሴሎና ሰማርያ፤* ቀደም ሲል በሰሜኑ ክፍል የአምልኮ ማእከል የነበሩ ናቸው የ7፥12፤ የዘፍ12፥6 ማብ፤ እንዲሁም ኢዮ24፥25-26 ይመ:: በ722-721 ዓ.ቅ.ክ ላይ የሰሜኑ መንግሥት ከጠፋ በኋላ፣ በተለይ በሕዝቅያስ (2ዜና 30፥11) እና በኢዮስያስ (2ዜና 34፥9 ይመ) የተሐድሶ እንቅስቃሴ ዘመን ብዙ እስራኤላውያን በየጊዜው ወደ ኢየሩሳሌም ጕዞ አድርገዋል:: *የእህል ቍርባንና ዕጣን፤* በኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ የነበረው መሠዊያ በመፈራረሱ ማቅረብ የተቻለው ደም አልባ መሥዋዕት ብቻ ነበር:: *እግዚአብሔር ቤት፤* ቤተ መቅደሱ የፈራረሰ ቢሆንም እንኳ ቦታው እስከ አሁን ድረስ ቅዱስ ተደርጎ ይቈጠራል::

41፥6 *እያለቀሰ፤* ከሰሜን የመጡትን ለቀስተኞች ሐዘን የሚካፈል በመምሰል ነው::

41፥7 *ከተማዪቱ፤* ምጽጳ ናት:: *በውሃ ማጠራቀሚያ*

ጋር የነበሩ ዐሥር ሰዎች ግን እስማኤልን፣ “እባክህ አትግደለን! በዕርሻችን ውስጥ የሸሸግነው ስንዴና ገብስ፣ የወይራ ዘይትና ማር ስላለን እባክህን አትግደለን” አሉት። እርሱም ተዋቸው፤ ከሌሎቹም ጋር አልገደላቸውም። 9እስማኤል ከጎዶልያስ በተጨማሪ የገደላቸው ሰዎች ሁሉ ሬሳ የተጣለበት የውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓድ ንጉሡ አሳ የእስራኤልን ንጉሥ ባአስን ስለ ፈራ ለመከላከል ያሠራው ነበር፤ ይህን ጕድጓድ፤ የናታንያ ልጅ እስማኤል በሬሳ ሞላው።

10እስማኤል በምጽጳ የቀረውን ሕዝብ ሁሉ ምርኮኛ አደረገ፤ እነርሱም የባቢሎን የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡረዘረዳን የአኪቃም ልጅ ጎዶልያስን በላያቸው ገዥ አድርጎ የሾመባቸው የንጉሡ ሴቶች ልጆችና በዚያ የቀሩት ሌሎች ሰዎች ሁሉ ነበሩ። የናታንያ ልጅ እስማኤል እነዚህን ማርኮ ወደ አሞናውያን ለመሻገር ተነሣ።

11የቃሬያ ልጅ ዮሐናና ከእርሱ ጋር የነበሩት የጦር መኰንኖች ሁሉ የናታንያ ልጅ እስማኤል የፈጸመውን ግፍ ሁሉ በሰሙ ጊዜ፣ 12የናታንያን ልጅ እስማኤልን ሊወጉ ሰዎቻቸውን ሁሉ ይዘው ሄዱ፤ በገባዖንም ባለው በታላቁ ኵሬ አጠገብ ደረሱበት። 13እስማኤል የያዛቸው ሰዎች ሁሉ የቃሬያን ልጅ ዮሐናንንና አብረውት የነበሩትን የጦር መኰንኖች ባዩ ጊዜ ደስ አላቸው። 14እስማኤል ከምጽጳ ማርኮ የወሰዳቸው ሰዎች ሁሉ አምልጠው ወደ ቃሬያ ልጅ ወደ ዮሐናን ገቡ። 15የናታንያ ልጅ እስማኤል ግን አብረውት ከነበሩት ስምንት ሰዎች ጋር ከዮሐናን አመለጠ፤ ሸሽቶም ወደ አሞናውያን ገባ።

## ሽሽት ወደ ግብፅ

16የቃሬያ ልጅ ዮሐናንና ከእርሱ ጋር የነበሩት የጦር መኰንንኖች ሁሉ የናታንያ ልጅ እስማኤል የአኪቃምን ልጅ ጎዶልያስን ከገደለ በኋላ፣ በምጽጳ ከማረካቸው የተረፉትን ሰዎች በማስመለስ ይዘው ሄዱ፤ እነዚህም፦ ወታደሮች፣ ሴቶች ሕፃናትና ከገባዖን ያመጧቸው የቤተ መንግሥት ባለ ሥልጣኖች ነበሩ። 17ከዚያም ተነሥተው ሄዱ፤ ወደ ግብፅም በማምራት በቤተልሔም አጠገብ ባለችው በጌሮት ከመዓም ዐረፉ፤ 18ወደ ግብፅም የሄዱት ከባቢሎናውያን[o] ለማምለጥ ነበር፤ ባቢሎናውያንንም የፈሩት የናታንያ ልጅ እስማኤል የባቢሎን ንጉሥ የምድሪቱ ገዥ አድርጎ የሾመውን የአኪቃምን ልጅ ጎዶልያስን በመግደሉ ነው።

# 42

የቃሬያን ልጅ ዮሐናንና የሆሻያን ልጅ ያእዛንያን[ሀ] ጨምሮ፣ የጦር መኰንኖች ሁሉ እንዲሁም ሕዝቡ ሁሉ ከትንሹ እስከ ትልቁ ቀርበው፣ 2ነቢዩ ኤርምያስን እንዲህ አሉት፤ “ቀድሞ ብዙዎች ነበርን አሁን እንደምታየን ግን የቀረነው ጥቂት ነን፤ ስለዚህ እባክህ ልመናችንን ስማ፤ ለዚህ ለተረፈው ሕዝብ ሁሉ ወደ አምላክህ ወደ *እግዚአብሔር* ጸልይ። 3አምላክህ *እግዚአብሔር* ወዴት መሄድ እንዳለብንና ምን ማድረግ እንደሚገባን እንዲነግረን ጸልይልን።”

4ነቢዩ ኤርምያስም፣ “ሰምቻችኋለሁ፤ እንዳላችሁት ወደ አምላካችሁ ወደ *እግዚአብሔር* በእርግጥ እጸልያለሁ፤ *እግዚአብሔር* ያለኝን ሁሉ አንዳች ሳላስቀር እነግራችኋለሁ” አላቸው።

5እነርሱም ኤርምያስን እንዲህ አሉት፤ “*እግዚአብሔር* አምላክህ በአንተ በኩል የሚልከውን ነገር ሁሉ ባናደርግ፣ *እግዚአብሔር* ራሱ በእኛ ላይ እውነተኛና ታማኝ ምስክር ይሁን። 6አምላካችንን *እግዚአብሔርን* በመታዘዝ መልካም ይሆንልን ዘንድ ነገሩ ቢስማማንም ባይስማማንም፣ አንተን ወደ እርሱ የምንልክህን አምላካችንን *እግዚአብሔርን* እንታዘዛለን።”

7ከዐሥር ቀን በኋላ የ*እግዚአብሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ መጣ። 8ስለዚህ የቃሬያን

41፥8 ኢሳ45፥3
41፥9 መሳ6፥2፤ 1ነገ15፥22፤2ዜና 16፥1:6
41፥10 ኤር38፥23፤ 40፥7:12:14
41፥11 ኤር40፥8
41፥12 ዘፀ14፥14፤ ኢሱ9፥3፤ዮሐ9፥7፤ 18፥36
41፥13 ቍ10
41፥14 ኤር40፥6
41፥15 ኢዮ21፥30፤ ምሳ28፥17
41፥16 ኢሳ1፥9፤ ኤር42፥1፤43፥2:4፤ ሕዝ7፥16፤14፥22፤ ሶፎ2፥9
41፥17 ዘፍ35፥19፤ 2ሳሙ19፥37፤ኤር 42፥14፤ሚክ 5፥2
41፥18 ዘኍ14፥9፤ 2ነገ25፥22፤ኢሳ 51፥12፤ኤር42፥16፤ ሉቃ12፥4-5
42፥1 ኤር6፥13፤ 40፥13፤41፥16፤ 44፥12
42፥2 ዘፍ20፥7፤ ዘሌ26፥22፤ኢሳ1፥9፤ ኤር36፥7፤ሰቆ1፥1፤ ሐሥ8፥24፤ያዕ5፥16
42፥3 ቍ20፤መዝ 86፥11፤ምሳ3፥6፤ኤር 15፥11
42፥4 ዘፀ8፥29፤ዘኍ 22፥18፤1ሳሙ3፥17 ፤12፥23፤ኤር1፥17
42፥5 ዘፍ31፥48፤ ዘዳ4፥26፤7፥9፤1ነገ 22፥16፤መዝ119፥ 160፤ኢሳ1፥2፤ዮሐ 8፥26፤ሮሜ1፥9፤3፥4፤ 1ቆሮ1፥9፤ራእ 1፥5
42፥6 ቍ19፤ዘፀ 24፥7፤ዘዳ5፥29፤ 6፥3፤ኢሱ24፥24፤ ኤር7፥23፤ 2፥15
42፥8 ቍ1፤ኤር 41፥16፤ማር9፥35፤ ሉቃ7፥28፤ዕብ8፥11

[o]18 ወይም *ከከለዳውያን*
[ሀ]1 የዕብራይስጡና የሰብዓ ሊቃናት ትርጕሞች (43፥2 ይመ) *አዛርያ* ይላሉ

ጕድጓድ፤ የሞተም ሆነ በሕይወት ያለ ወንጀለኛ የሚጣልበት ወይም በእስር የሚቈይበት ቦታ ነው (37፥16 እና ማብ 38፥6 ይመ)።

41፥8 *ስንዴና ገብስ የወይራ ዘይትና ማር፤* እስማኤል ወደ አሞን በሸሸ ጊዜ (ቍ15) ይዞት የሄደው ሥንቅ ሊሆን ይችላል።

41፥9 *ንጉሡ አሳ ... ያሠራው፤* ጠላት ከበባ በሚያደርግበት ጊዜ ውሃ ለማጠራቀም ጕድጓዶች አስፈላጊ ስለ ነበሩ፣ አሳ በምጽጳ ምሽግ በሚያሠራበት ጊዜ ጕድጓዶችን ማስቈፈር የሥራው አንዱ ክፍል ነበር (1ነገ15፥22 ይመ)። የታሪክ ቅርስ ተመራማሪዎች ከጥንታዊ የምጽጳ ከተማ ፍራሽ ውስጥ ብዙ የውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓዶችን አግኝተዋል።

41፥10 *የንጉሡ ሴቶች ልጆችና፤* የንጉሡ ሴዴቅያስ የራሱ ልጆች ብቻ ሳይሆኑ በቤተ መንግሥቱ ውስጥ በቤተ ሰብነት ይኖሩ የነበሩ ሴቶች ሊሆኑ ይችላል (የ36፥26 ማብ ይመ)። *አሞናውያን፤* 40፥14 እና ማብ ይመ።

41፥12 *በገባዖንም ባለው በታላቁ ኵሬ፤* በ2ሳሙ2፥13 ላይ የተጠቀሰው ዐይነት ሊሆን ይችላል።

41፥15 *ስምንት ሰዎች ጋር ... አመለጠ፤* ከዮሐናን ጋር ባደረገው ውጊያ፣ ለእስማኤል የሞቱበት ሁለት ሰዎች ብቻ ነበሩ (ቍ2 ይመ)።

41፥17 *በጌሮት ከምዓም፤* ቦታው የት እንደሚገኝ አይታወቅም፤ ምናልባት አቤሴሎም ከሞተ በኋላ አብሮት ወደ ኢየሩሳሌም የተመለሰው የዳዊት ጓደኛ የነበረው የከመዓም “ማረፊያ ቦታ” ሊሆን ይችላል (2ሳሙ19፥37-40)።

42፥1 *የሆሻያን ልጅ ያእዛንያን፤* ምናልባት፣ “የማዕካታዊው ልጅ ያእዛንያ” የተባለው ሰው ይሆናል (40፥8)። ያእዛንያም ልክ እንደ ንጉሥ ዖዝያን (2ነገ14፥21፤ 2ዜና26፥1 ይመ) ዓዛርያስ በሚል ስም ይጠራ ነበር (43፥2)።

42፥2 *ኤርምያስን፤* በምጽጳ ከነበሩት ከሕዝቡ ቅሬታዎች መካከል አንዱ ሳይሆን አይቀርም (41፥16)። *ልመናችንን ስማ፤* ቍ9፤ 37፥20 ይመ።

*42፥3፤* ሕዝቡ እግዚአብሔርን የሚጠይቁት፣ ብቸኛ ምርጫቸው በማድረግ አጽንተው ለያዙት ወደ ግብፅ የመሄድ ጕዳይ (ቍ17፤ 41፥17 ይመ) ማረጋገጫ ለማግኘት ነው።

42፥6 *አምላካችንን እግዚአብሔርን እንታዘዛለን፤* የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለማድረግ ያላቸውን መሻት እዚህ ላይ ሁለት ጊዜ ቢናገሩትም እንኳ፣ የራሳቸውን ምኞት ለመከተልም ፈጥነው መወሰናቸውን ይገልጻሉ (43፥2 ይመ)።

42፥7 *ከዐሥር ቀን በኋላ፤* ራሱ እርግጠኛ እስከሚሆን ድረስ ኤርምያስ የእግዚአብሔርን ቃል ወደ ሕዝቡ አያመጣም

ልጅ ዮሐናንንና፣ ከእርሱም ጋር የነበሩትን የጦር መኰንኖች ሁሉ እንዲሁም ሕዝቡን ሁሉ ከትንሽ እስከ ትልቅ ጠርቶ፤ [9]እንዲህ አላቸው፤ “ልመናችሁን በፊቱ እንዳቀርብ ወደ እርሱ የላካችሁኝ የእስራኤል ስምላክ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ [10]‘በመባሁባ ችሁ ጥፋት አዝኛለሁና በዚህች ምድር ብትቀመጡ እሠራችኋለሁ እንጂ አላፈርሳ ችሁም፤ እተክላችኋለሁ እንጂ አልነቅላች ሁም። [11]አሁን የሚያስፈራችሁን የባቢሎንን ንጉሥ አትፍሩ፤ አድናችሁ ዘንድ ከእጁም አስጥላችሁ ዘንድ፤ እኔ ከእናንተ ጋር ነኝና አትፍሩ ይላል *እግዚአብሔር*፤ [12]እርሱ እን ዲምራችሁና ወደ አገራችሁ እንዲመልሳ ችሁ እኔ እምራችኋለሁ።’

[13]“እናንተ ግን፤ ‘በዚህች ምድር አንቀ መጥም’ ብትሉና ስምላካችሁን *እግዚአብሔ ርን* ባትታዘዙ፣ [14]ደግሞም፣ ‘ጦርነት ወደ ማናይበት፣ የመለከት ድምፅ ወደማንሰማ በትና ወደማንራብበት ወደ ግብፅ ምድር ሄደን በዚያ እንኖራለን’ ብትሉ፣ [15]እንግ ዲህ የይሁዳ ቅሬታ ሆይ፤ *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ፤ የእስራኤል ስምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ‘ወደ ግብፅ ለመሄድ ወስናችሁ እዚያ ለመቀመጥ ብትሄዱ፣ [16]የፈራችሁት ሰይፍ በዚያ ያገ ኛችኋል፤ የሠጋችሁበት ራብ እስከ ግብፅ ድረስ ተከትሎአችሁ ይመጣል፤ በዚያም ትሞታላችሁ። [17]በዚያም ለመኖር ወደ ግብፅ ለመሄድ የወሰኑ ሁሉ በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር በእርግጥ ይሞታሉ፤ ከማመጣባቸ ውም ጥፋት አንድ እንኳ የሚተርፍ ወይም የሚያመልጥ አይገኝም።’ [18]የእስራኤል ስም ላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፦ ‘ቍጣዬና መዓቴ በኢየሩሳሌም በሚኖ ሩት ሁሉ ላይ እንደ ፈሰሰ፣ እንዲሁ ወደ ግብፅ በገባችሁ ጊዜ መዓቴ በእናንተ ላይ ይፈሳል፤ እናንተም የመነቀፊያና የድንጋጤ፣ የመረገሚያና የመዘባበቻ ምልክት ትሆናላ ችሁ፤ ይህንም ስፍራ ዳግመኛ አታዩም።’

[19]“እናንተ የይሁዳ ቅሬታ ሆይ፤ *እግዚ አብሔር*፣ ‘ወደ ግብፅ አትሂዱ’ ብሎአች ኋል፤ እኔም ዛሬ እንዳስጠነቀቅኋችሁ በእር ግጥ ዕወቁ፤ [20]‘ወደ ስምላካችን ወደ *እግዚ አብሔር* ጸልይልን፤ እርሱ ያለህን ሁሉ ንገረን፤ እኛም እንታዘዛለን’ ብላችሁ ወደ ስምላካችሁ ወደ *እግዚአብሔር* በላካችሁኝ ጊዜ ሕይወታችሁን የሚያጠፋ ስሕተት[*] ፈጸማ ችሁ። [21]እነሆ፤ ዛሬ በግልጥ ነገርኋችሁ፤ እናንተ ግን *እግዚአብሔር* ስምላካችሁ ልኮኝ የነገርኋችሁን ሁሉ አሁንም አልታዘዛችሁም፤ [22]እንግዲህ ሄዳችሁ ልትኖሩበት በፈለጋች ሁት ስፍራ በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር እን ደምትሞቱ በእርግጥ ዕወቁ።”

# 43

ኤርምያስ፣ *እግዚአብሔር* ለእነርሱ እንዲነግራቸው የላከውን የስምላካቸ ውን *የእግዚአብሔርን* ቃል ሁሉ ለሕዝቡ ተናግሮ በጨረሰ ጊዜ፣ [2]የሆሽያ ልጅ ዓዛ ርያስ፣ የቃሬያ ልጅ ዮሐናንና ትዕቢተኞች የሆኑ ሰዎች ሁሉ ኤርምያስን እንዲህ አሉት፤ “ትዋሻለህ! ስምላካችን *እግዚአብሔር* ‘እዚያ ለመኖር ወደ ግብፅ አትሂዱ’ ብለህ ንገራቸው’ ብሎ አልላከህም፤ [3]ነገር ግን ባቢሎናውያን እንዲገድሉን ወይም ማርከው ወደ ባቢሎን እንዲወስዱን ለእነርሱ[*] አሳ ልፎ ትሰጠን ዘንድ የኔርያ ልጅ ባሮክ በእኛ ላይ አነሣሥቶሃል።”

[4]ስለዚህ የቃሬያ ልጅ ዮሐናንና፣ የጦር መኰንኖቹ ሁሉ እንዲሁም ሕዝቡ በሙሉ *እግዚአብሔር* በይሁዳ ምድር እንዲቀመጡ ያዘዛቸውን ቃል አልሰሙም። [5]ነገር ግን፣ የቃሪያ ልጅ ዮሐናንና የጦር መኮንኖቹ ሁሉ፣ በይሁዳ ምድር ለመቀመጥ ከተበተ ኑበት ከአሕዛብ ሁሉ መካከል የተመለሱ ትን የይሁዳን ቅሬታዎች ሁሉ ይዘው ሄዱ፤ [6]በተጨማሪም ወንዶችን፣ ሴቶችንና ሕፃና ትን እንዲሁም የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡ ዘረዳን በአኪቃም ልጅ በጎዶልያስ እጅ የተዋቸውን የንጉሡን ሴቶች ልጆች፣ ነቢዩ ኤርምያስንና የኔርያን ልጅ ባሮክን ወሰ ዷቸው፤ [7]*የእግዚአብሔርንም* ቃል ባለመታ ዘዝ ወደ ግብፅ ገቡ፤ ዘልቀውም እስከ ጣፍ ናስ ድረስ ሄዱ።

[8]በጣፍናስም *የእግዚአሔር* ቃል ወደ ኤርምያስ እንዲህ ሲል መጣ፤ [9]“ትልልቅ ድንጋዮች ውሰድና በጣፍናስ ባለው የፈር ዖን ቤተ መንግሥት በር ላይ የይሁዳ ሰዎች

42፥9 ቍ2፤2ነገ 22፥15
42፥10 ዘዳ29፥28፤ 30፥9፤2ዜና34፥24፤ መክ3፥2፤ኢሳ30፥26፤ ኤር18፥8፤24፥6፤ 43፥4፤ 45፥4፤ሕዝ 36፥36፤ዳን 1፥4
42፥11 ዘኍ14፥9፤ 1ሳሙ15፥24፤መዝ 3፥7፤18፥27፤23፥4፤ 69፥35፤119፥94፤ምሳ 20፥22፤ኢሳ63፥1፤ ኤር1፥8፤27፥11፤ማቴ 10፥28፤ሮሜ8፥31፤ 2ጢሞ1፥7፤ዕብ7፥25
42፥12 ዘፍ31፥3፤ ዘፀ3፥21፤2ሳሙ24፥ 14፤ነህ1፥9፤መዝ106፥ 44-46፤2ቆሮ1፥3
42፥13 ዘዳ11፥28
42፥14 ዘኍ11፥4-5 ፤ዘዳ8፥3፤17፥16፤ኢሱ 6፥20፤1ሳሙ2፥5፤ምሳ 10፥3፤ኢሳ30፥2፤65፥ 13፤ማቴ4፥2-4፤ 24፥31
42፥15 ኤር44፥24
42፥16 ዘፍ41፥55፤ 2፥17፤ዘሌ26፥33፤2ዜ ና25፥4፤ኢዮ21፥20፤ ኤር41፥18፤ሕዝ3፥19 ፤11፥8፤14፥17፤18፥4
42፥17 ቍ22፤ኤር 21፥7፤44፥13
42፥18 ዘኍ5፥27፤ ዘዳ28፥25፡37፤29፥18 -20፤2ዜና12፥7፤ 36፥19፤መዝ44፥13፤ ኤር22፥10፤25፥18፤ 39፥1-9
42፥19 ቍ6፤ዘዳ 17፥16፤ኢሳ30፥7፤ ኤር40፥15፤43፥2፤ 44፥16
42፥20 ቍ2፤ሕዝ 14፥7-8
42፥21 ዘፀ24፥7፤ ኤር40፥3፤ሕዝ2፥7፤ 12፥2፤ዘካ7፥11-12
42፥22 ቍ17፤ኢሳ 1፥28፤ኤር15፥2፤ 24፥10፤ሕዝ6፥11፤ ሆሴ9፥6
43፥1 ኤር26፥8፤ 42፥9-22
43፥2 ዘፍ19፥14፤ ዘፀ24፥7፤ዘዳ 13፥3፤ 2ነገ25፥24፤ነህ9፥29፤ ኤር18፥19፤40፥16፤ 41፥16፤42፥19፤ሕዝ 37፥14፤ሮሜ9፥1፤ 1ቆሮ4፥18-21፤2ቆሮ 11፥31፤1ጢሞ2፥7

43፥3 ኤር32፥12፤38፥4፤41፥18፤52፥30 43፥4 2ዜና25፥16፤ ኤር41፥16፤42፥5-6፡10 43፥5 ኤር40፥12 43፥6 ኤር6፥12፤ 32፥12 43፥7 2ነገ25፥26፤ኤር2፥16፤44፥1፤46፥14፤ሕዝ30፥18 43፥8 መዝ139፥7፤ኤር2፥16 43፥9 ዘፍ11፥3፤31፥45-53፤47፥14 ፤ኢሱ4፥1-7፤1ነገ18፥31-32

[*]20 *ወይም በልባችሁ ስሕተት ሠራችሁ*

ነበር (28፥10-12 ይመ)።

42፥10 *እሠራችኋለሁ ... አላፈርሳችሁም እተክላችኋለሁ ... አልነቅላችሁም፤* 1፥10 እና ማብ፤ እንዲሁም 31፥4፡28፤33፥7 ይመ።

42፥12 *እርሱ እንዲምራችሁና፤* ይህን የሚመስል ሐሳብ በዘፍ43፥14፤ በ1ነገ8፥50 ላይ ይመ።

42፥16 *የፈራችሁት ሰይፍ በዚያ ያገኛችኋል፤* 43፥11 እና ማብ ይመ።

*42፥17-18፤* 44፥11-14 ይመ።

42፥17 *በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር፤* የ14፥12 ማብ ይመ።

42፥18 *ቍጣዬና መዓቴ ... እንደ ፈሰሰ፤* 7፥20፤ 44፥6 ይመ። *የመነቀፊያና ... የመረገሚያና፤* የ24፥9፤ 25፥18 ማብ 29፥18 ይመ። *ይህንም ስፍራ፤* ኢየሩሳሌምን ማለት ነው።

42፥19 *እንዳስጠነቀቅኋችሁ፤* 11፥7 ይመ።

43፥2 *ዓዛርያስ፤* የ42፥1 ማብ ይመ። *ትዕቢተኞች የሆኑ ሰዎች፤* እንደዚህ ዐይነት ሰዎች መሆናቸውን የገለጹት ከአነጋገራቸው የተነሣ ነው።

43፥3 *ባሮክ፤* የ32፥12 ማብ ይመ። የኤርምያስ ተቃዋሚዎች በመንፈሳዊ አቋም እንደ ኤርምያስ ጠንካራና ታዋቂ አይደለም ብለው የሚያስቡትን ሰው ጥፋተኛ ለማድረግ ፈለጉ።

43፥6 *የንጉሡን ሴቶች ልጆች፤* የ41፥10 ማብ ይመ። *ኤርምያስንና ... ባሮክን፤* በ32፥6-15፤ 40፥1-6፤ 42፥13-22 ላይ የተጠቀሰውን ሐሳብ ግምት ውስጥ በማስገባት ከፈቃዳቸው ውጭ ወደ ግብፅ እንደ ሄዱ አያጠራጥርም።

43፥7 *ጣፍናስ፤* የ2፥16 ማብ ይመ።

43፥9 *የፈርዖን ቤተ መንግሥት፤* ዋና መኖሪያው ላይሆን ይችላል። በኤሌፋንታይን በፓፒረስ ላይ ተጽፈው ከተገኙት ጽሑ

እያዩ በሸክላ ጡብ ወለል ውስጥ ቅበራቸው፤ [10]እንዲህም በላቸው፤ 'የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ አገልጋዬን የባቢሎንን ንጉሥ ናቡከደነፆርን እንዲመጣ አደርጋለሁ፤ ዙፋኑንም እዚህ በቀበርኋቸው ድንጋዮች ላይ እዘረጋለሁ፤ የንጉሥ ድንኳኑንም በላያቸው ይተክላል:: [11]እርሱም መጥቶ ግብፅን ይወጋል፤ ሞት የሚገባቸውን ለሞት፣ ለምርኮ የተመደቡትን ወደ ምርኮ፣ ለሰይፍ የተዳረጉትን ለሰይፍ አሳልፎ ይሰጣል:: [12]እርሱ የግብፅ አማልክት ቤተ ጣዖቶች ላይ እሳት ይለኩሳል፤ ያቃጥላቸዋልም፣ አማልክታቸውንም ማርኮ ይወስዳል:: እረኛ ልብሱን እንደሚጐናጸፍ የግብፅን ምድር ተጐናጽፎ ከዚያ በሰላም ይሄዳል::[፬] [13]በግብፅ ምድር የሚገኙትን የፀሓይ[፭] አምላክ ቤተ ጣዖት ሐውልቶች ይሰባብራል፤ የግብፅንም አማልክት ቤተ ጣዖቶች በእሳት ያቃጥላል::'

## ጣዖትን ማምለክ ያስከተለው ጥፋት

**44** በግብፅ ሰሜናዊ ክፍል በሚግዶል፣ በጣፍናስና በሜምፎስ[፮] እንዲሁም በግብፅ ደቡባዊ ክፍል[፯] ስለሚኖሩት የአይሁድ ሕዝብ እንዲህ የሚል ቃል ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ ኤርምያስ መጣ፤ [2]"የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ በኢየሩሳሌምና በይሁዳ ከተሞች ሁሉ ላይ ያመጣሁትን ታላቅ ጥፋት አይታችኋል፤ ዛሬ ማንም የማይኖርባቸው ባድማ ሆነው ይታያሉ፤ [3]ይህም የሆነው ስላደረጉት ክፋት ነው:: እነርሱም ሆኑ እናንተ ወይም አባቶቻችሁ ላላወቋቸው ለሌሎች አማልክት በማጠንና በማምለክ አስቈጥተውኛል:: [4]እኔም፣ 'ይህን የምጠላውን አስጸያፊ ነገር አታድርጉ' በማለት አገልጋዮቼን ነቢያትን ደጋግሜ ላክሁባቸው:: [5]እነርሱ ግን አልሰሙም፤ ልብም አላሉም፤ ከክፋታቸው አልተመለሱም፤ ለሌሎችም አማልክት ማጠን አልተውም:: [6]ስለዚህ መዓቴና ቍጣዬ ፈሰሰ በይሁዳ ከተሞችና በኢየሩሳሌም መንገዶች ላይ ነደደ፤ ዛሬ እንደሚታዩትም ማንም የማይኖርባቸው ፍርስራሾች አደረጋቸው::

[7]"አሁንም የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'ዘር እንዳይቀርላችሁ ወንዶችና ሴቶች፣ ልጆችና ሕፃናት በይሁዳ እንዳይገኙ ለምን እንዲህ ዐይነት ታላቅ ጥፋት በራሳችሁ ላይ ታመጣላችሁ? [8]ልትኖሩባት በመጣችሁባት በግብፅ ምድር ለሌሎች አማልክት በማጠን፣ እጆቻችሁ ባበጇቸው ነገሮች ለምን ታስቈጡኛላችሁ? በምድር ባሉት ሕዝቦች ሁሉ ዘንድ የርግማንና የመዘባበቻ ምልክት ለመሆን ራሳችሁን ታጠፋላችሁን? [9]በይሁዳ ምድርና በኢየሩሳሌም መንገዶች አባቶቻችሁ የይሁዳ ነገሥታትና ሚስቶቻቸው፣ እንዲሁም እናንተና ሚስቶቻችሁ ያደረጋችሁትን ክፋት ረስታችሁታልን? [10]እስከ ዛሬ ድረስ ራሳቸውን ዝቅ በማድረግ ክብርን አልሰጡኝም፤ በእናንተና በአባቶቻችሁ ፊት ያኖርሁትንም ሕጌንና ሥርዐቴን አልተከተሉም::'

[11]"ስለዚህ የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'በእናንተ ላይ ጥፋት ለማምጣትና ይሁዳን ሁሉ ለመደምሰስ ቈርጬ ተነሥቻለሁ:: [12]ሄደው በግብፅ ለመቀመጥ የወሰኑትን የይሁዳ ቅሬ

43፥10 መዝ18፥11፤ኢሳ44፥28፤45፥1፤ኤር25፥9፤27፥6፤46፥13፤49፥38
43፥11 ዘዳ28፥64፤ምሳ11፥19፤መዝ49፥14፤ኤር15፥2፤46፥13-26፤ሕዝ29፥19-20፤32፥11፤ዘካ11፥9፤ሮሜ6፥23፤ዕብ 9፥27፤ራእ13፥10
43፥12 ቍ13፤ ዘፀ12፥12፤ኢሱ7፥15፤1ነገ16፥32፤መዝ104፥2፤109፥18-19፤ኢሳ2፥18፤ኤር46፥25፤ሕዝ30፥13፤ዳን11፥8፤ዘካ13፥2
43፥13 ዘኍ1፥16፤ዘዳ4፥19፤ኢሳ19፥18፤ኤር52፥17፤ሕዝ26፥11
44፥1 ዘፀ14፥2፤ዘዳ32፥42፤ኢሳ11፥11፤19፥13፤ኤር43፥7፡8፤24፥8
44፥2 ዘሌ26፥31፤ዘዳ29፥23፤2ዜና34፥24፤ኢሳ6፥11፤ኤር40፥5
44፥3 ቍ8፤ዘፀ32፥22፤ዘኍ11፥33፤16፥40፤25፥3፤ዘዳ13፥6-11፤29፥26፤መሳ2፥19፤ኢሳ19፥1
44፥4 ዘኍ11፥29፤ዘዳ18፥9፤1ነገ14፥24፤ኤር7፥13፤1ጴጥ4፥3
44፥5 ቍ21፤ዘፍ6፥5፤ ኤር1፥16፤11፥8-10፤25፥4፡7፤ሕዝ8፥11፤16፥18፤23፥41፤ዳን9፥6፤ሮሜ1፥18፤2ጢሞ2፥19
44፥6 ዘሌ26፥31፡34፤ዘዳ29፥23፤ሰቆ1፥13፤ሕዝ8፥18፤20፥34፤ዘካ7፥14
44፥7 2ነገ21፥14፤ኤር26፥19፤51፥22
44፥8 ቍ3፡17-25፤ዘፀ12፥12፤መዝ44፥13፤ኢሳ40፥18-20፤ኤር10፥3፤41፥5፤ሮሜ1፥23፤1ቆሮ10፥22 44፥9 ቍ17፡21፤መሳ2፥19፤1ነገ21፥25፤2ነገ23፥11፤ምሳ31፥10፤ኤር6፥12፤11፥12፤32፥32
44፥10 ዘሌ18፥4፤ዘዳ6፥13፤8፥3፤1ነገ9፥6-9፤2ነገ17፥17፤ኢሱ1፥7፤መዝ5፥7፤ኤር11፥8፤ማቴ5፥17-20፤23፥12፤ገላ3፥19፤ፊል2፥8፤1ዮሐ3፥4 44፥11 2ዜና34፥24፤አሞ9፥4፤ራእ4፥8 44፥12 ቍ7፤ዘዳ28፥25፤ኢሳ1፥28፤ኤር29፥18፤40፥15፤42፥1

[፫]3 ወይም *ከለዳውያን*
[፬]12 ወይም *እኔ እለኩሳለሁ፤ ... አቃጥላለሁ፤ ... እወስዳለሁ፤*
[፭]13 ወይም *በሔሊዮፖሊስ/ በፀሓይ ከተማ*
[፮]1 ዕብራይስጡ *ኖፍ* ይላል
[፯]1 ዕብራይስጡ *ከፌትሮስ* ይላል

ፎች አንዱ፣ "የንጉሡ ቤት" ፈርዖን ደቡብ ግብፅ የምትገኘውን ኤሌፋንታይንን በሚጐበኝበት ጊዜ ያረፈበት ፀጥ ያለ ቤተ መንግሥት እንደ ሆነ ይገልጣል::

43፥10 *አገልጋዬን ... ናቡከደነፆርን፤* የ25፥9 ማብ ይመ:: *ዙፋኑንም፤* ሥልጣኑን ያመለክታል::

*43፥11፤* 15፥2 እና ማብ ይመ፤ ሕዝ29፥17-20 እና ማብ ይመ::

43፥12 *እረኛ ልብሱን እንደሚጐናጸፍ ... ተጐናጽፎ፤* በልበ ሙሉነት እንደሚያደርገው ያመለክታል::

43፥13 *በግብፅ ምድር የሚገኙትን የፀሓይ አምላክ ቤተ ጣዖት፤* በቀጥታ "በግብፅ የሚገኘው ቤት ሳሚስ" ማለት ነው፤ ይህም በይሁዳ ከሚገኘው "ቤት ሳሚስ" (2ነገ14፥11) የተለየ መሆኑን የሚገልጽ ሐረግ ይዞአል:: የግብፁ ከተማ ምናልባት በዕብራይስጥ ሔሊዮፖሊስ (የዘፍ41፥45 ማብ ይመ) ተብሎ ከሚጠራው ጋር የሚቃረብ (የሚዛመድ) ይሆናል:: *ሐውልቶች፤* ጥንታዊ ሔሊዮፖሊስ ታዋቂ እንድትሆን ያደረጓት ዐምዶች ናቸው::

*44፥1-30፤* ከኤርምያስ ትንቢቶች የጽሑፉ ሥራ የመጨረሻ ክፍል ይህ ነው 9የ40፥1-44፥30 ይመ)::

44፥1 *በግብፅ ... ስለሚኖሩት የአይሁድ ሕዝብ፤* ከዚያ በፊት ተገደው ከአገር እንዲወጡ (እንዲሰደዱ) የተደረጉትን (ለምሳ:- 2ነገ23፥34) እና ወይም ደግሞ በ43፥5-7 ላይ የተጠቀሱትን አይሁድ የሚመለከት ሳይሆን አይቀርም፤ ያም ሆነ ይህ በቍ 15 ላይ የተጻፈውን እውን ለማድረግ በም 43 እና 44 መካከል የጊዜ ክፍተት ሳይኖር አልቀረም:: *በሚግዶል፤* ይህ ቦታ የት እንደ ሆነ በውል ተለይቶ የሚታወቅ ነገር የለም፤ ምናልባትም በሰሜኑ የግብፅ ምድር የሚገኝ ቦታ ሳይሆን አይቀርም (46፥14 ይመ):: ትርጕሙ "ማማ" ማለት ነው:: *በጣፍናስና በሜምፎስ፤* የ2፥16፤ የኢሳ19፥13 ማብ ይመ::

*44፥3፤* የ1፥16 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 11፥17፤ 19፥4፤ 32፥32 ይመ::

*44፥4፤* የ7፥25 ማብ ይመ::

44፥6 *መዓቴና ቍጣዬ ፈሰሰ፤* 7፥20፤ 42፥18 ይመ::

44፥7 *ታላቅ ጥፋት በራሳችሁ ላይ ታመጣላችሁ፤* 26፥19 ይመ:: *ወንዶችና ሴቶች፣ ልጆችና ሕፃናት፤* በአጠቃላይ "እያንዳንዱን ሰው" የሚያመለክት ሐረግ (1ሳሙ15፥3፤ 22፥19 ይመ)::

44፥8 *እጆቻችሁ ባበጇቸው ነገሮች፤* ጣዖቶች ናቸው (1፥16 እና ማብ ይመ):: *የርግማንና የመዘባበቻ ምልክት፤* 42፥18 ይመ፤ እንዲሁም የ24፥9፤ የ25፥18 ማብ ይመ::

44፥9 *ነገሥታትና ... ሚስቶቻችሁ ያደረጋችሁትን ክፋት፤* ከባለቤቶቻቸው ጋር "የሰማይ ንግሥት" የተባለችውን ያመለኩ (ቍ19፤ እንዲሁም ቍ15 ይመ)::

44፥10 *ሕጌንና ሥርዐቴን አልተከተሉም፤* 9፥13፤ 26፥4 ይመ፤ እንዲሁም 7፥9 እና ማብ ይመ::

*44፥11-14፤* 42፥17-18 እና ማብ ይመ::

44፥11 *ተነሥቻለሁ፤* ይህ በዕብራይስጥ ቃል በቃል ሲተረጐም "ፊቴን በ ... ላይ አደርጋለሁ" ማለት ነው (21፥10

ታዎች ሁሉ እንተቃለሁ፤ ሁሉም ይጠፋሉ፤ በግብፅ ምድር በሰይፍ ይወድቃሉ፤ በራብ ያልቃሉ፤ ከትንሽ እስከ ትልቅ በሰይፍና በራብ ይሞታሉ፤ የመነቀፊያና የድንጋጤ፣ የመረገሚያና የመዘባበቻ ምልክት ይሆናሉ:: [13]ኢየሩሳሌምን እንደቀጣሁ፣ በግብፅ የሚኖሩትን በሰይፍ፣ በራብና በቸነፈር እቀጣለሁ፤ [14]ወደ ግብፅ የመጡት የይሁዳ ቅሬታዎች ወደ ይሁዳ ለመመለስ ቢመኙም ከጥቂት ስደተኞች በስተቀር አምልጦ ወይም ተርፎ ወደ ይሁዳ የሚመለስ አንድም ሰው አይኖርም::' "

[15]ሚስቶቻቸው ለሌሎች አማልክት ማጠናቸውን ያወቁ ወንዶች ሁሉና በዚያ የነበሩት ሴቶች ሁሉ ይህም ማለት በሰሜንና በደቡብ ግብፅ[ሠ] የሚኖረው ሕዝብ ሁሉ ታላቅ ጉባኤ ሆነው ለኤርምያስ እንዲህ አሉት፤ [16]"አንተ *በእግዚአብሔር* ስም የነገርኸንን መልእክት አንሰማም፤ [17]እናደርጋለን ያልነውን ሁሉ እናደርጋለን፤ አባቶቻችን፣ ነገሥታታችንና ባለ ሥልጣኖቻችን በይሁዳ ከተሞችና በኢየሩሳሌም መንገዶች እንዳደረጉት ሁሉ እኛም ለሰማይዋ ንግሥት እናጥናለን፤ የመጠጥ ቍርባን እናፈስላታለን:: በዚያን ጊዜ የተትረፈረፈ ምግብ ነበረን፤ በመልካም ሁኔታ እንገኝ ነበር እንጂ ምንም ክፉ ነገር አልገጠመንም:: [18]ነገር ግን ለሰማይዋ ንግሥት ማጠንና የመጠጥ ቍርባን ማፍሰስ ከተውን ወዲህ፣ ሁሉን ነገር አጥተናል፤ በሰይፍና በራብም እያለቅን ነው::

[19]ሴቶቹም፣ "ለሰማይዋ ንግሥት በምናጥንበት ጊዜና የመጠጥ ቍርባን በምናፈስበት ጊዜ የጋገርነውንና እንደ ምስሏ ያለ ዕንጐቻ ያፈሰስነውንም የመጠጥ ቍርባን ባሎቻችን ሳያውቁት ኖሮአልን?" አሉ::

[20]ኤርምያስ ይህን መልስ ለሰጠው ሕዝብ፣ ለወንዶችና ለሴቶች ሁሉ እንዲህ አለ፤ [21]"እናንተና አባቶቻችሁ፣ ነገሥታታችሁና ባለሥልጣኖቻችሁ እንዲሁም የምድሪቱ ሕዝብ በይሁዳ ከተሞችና በኢየሩሳሌም መንገዶች ያጠናችሁትን እግዚአብሔር የማያስታውሰውና የዘነጋው ይመስላችኋልን? [22]*እግዚአብሔር* ክፉ አድራጎታችሁንና አስጸያፊ ተግባራችሁን ሊታገሥ ባለመቻሉ፣ ዛሬ እንደ ሆነው ምድራችሁ የርግማን ምልክት፣ ሰው የማይኖርበት ባዶ ምድረ በዳ ሆኖአል:: [23]ዕጣን በማጠን *በእግዚአብሔር* ላይ ኀጢአት ስለ ሠራችሁና ቃሉን ስላልጠበቃችሁ ሕጉን፣ ሥርዐቱንና ትእዛዙን ስላላከበራችሁ ዛሬ እንደምታዩት ጥፋት መጥቶባችኋል::"

[24]ኤርምያስም ለሕዝቡና ለሴቶቹ ሁሉ እንዲህ አለ፤ "በግብፅ የምትኖሩ የይሁዳ ሕዝብ ሁሉ፤ *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ:: [25]የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ እናንተና ሚስቶቻችሁ፣ 'ለሰማይዋ ንግሥት ለማጠንና የመጠጥ ቍርባን ለማፍሰስ የተሳልነውን ስእለታችንን በእርግጥ እንፈጽማለን' ብላችሁ የገባችሁትን ቃል በተግባር አሳይታችኋል::'

"እንግዲያውስ ወደ ኋላ አትበሉ፤ ቃል የገባችሁትን፤ ስእለታችሁንም ፈጽሙ:: [26]በግብፅ የምትኖሩ አይሁድ ሁሉ *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ፤ '*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል "ከእንግዲህ ወዲህ በየትኛውም የግብፅ ክፍል የሚኖር ማንኛውም አይሁዳዊ፣ '*ሕያው እግዚአብሔርን!*' ብሎ ስሜን እንዳይጠራ፣ እንዳይምልም በታላቁ ስሜ ምያለሁ፤ [27]ለመልካም ሳይሆን ለክፉ እተጋባቸዋለሁና፤ በግብፅ የሚኖሩ አይሁድ ፈጽሞ እስኪጠፉ ድረስ በሰይፍና በራብ ይደመሰሳሉ:: [28]ከሰይፍ አምልጠው፣ ከግብፅ ወደ ይሁዳ ምድር የሚመለሱት በጣም ጥቂት ሰዎች ይሆናሉ:: በግብፅ ምድር ለመኖር የመጡት የይሁዳ ቅሬታ ሁሉ፣ ከእኔ ወይም ከእነርሱ የማንኛችን ቃል እንደሚጸና ያውቃሉ::

[29]" 'በእናንተ ላይ አመጣለሁ ያልሁትን ክፉ ነገር እንደሚፈጸም ታውቁ ዘንድ በዚህ ስፍራ እንደምቀጣችሁ ይህ ምልክት ይሆናችሁ' ይላል *እግዚአብሔር*:: [30]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል:- 'የይሁዳን ንጉሥ ሴዴቅያስን ሊገድለው ለፈለገው ጠላቱ ለባቢሎን

44፥13 ዘፀ32፥24፤ ዘሌ26፥14-17፤ኤር 15፥2፤42፥17
44፥14 ኤር22፥24-27፤49፥5፤ሰቆ4፥15፤ ሕዝ6፥8፤ሮሜ9፥27
44፥15 ዘፍ3፥6፤ ምሳ31፥10፤ኢሳ11፥11፤ኤር6፥12፤18፥15 ፤1ጢሞ2፥14
44፥16 1ሳሙ8፥19 ፤ኢዮ15፥25-26፤ኤር 11፥8-10፤42፥19
44፥17 ቍ9:25:28 ፤ዘፀ16፥3፤ዘኍ11፥4-6፤ዘዳ23፥23፤ነህ9፥34 ፤ኢዮ21፥15፤ኢሳ3፥9፤ 65፥3፤ኤር2፥26፤11፥ 12፤ሆሴ2፥5-13፤9፥1፤ ዘካ 1፥6
44፥18 ዘሌ23፥18፤ ኤር42፥16፤ሚል 3፥13-15
44፥19 ዘፍ3፥6፤ዘሌ 7፥12፤26፥1፤ኤር18፥ 15፤7፥18፤ሐሥ17፥29 ፤ኢፌ5፥22
44፥21 ቍ9፤መዝ 79፥8፤ኢሳ64፥9፤ኤር 2፥26፤11፥13፤14፥10 ፤ሆሴ8፥13
44፥22 ዘፍ19፥13፤ ዘሌ26፥31:32፤መዝ 107፥33-34፤ኢሳ1፥ 14፤ኤር25፥18፤ሕዝ 33፥28-29
44፥23 ዘሌ18፥4፤ 26፥33፤1ነገ9፥6:9፤ ኤር7፥13-15፤40፥2 ፤ሕዝ39፥23፤ዳን 9፥11-12
44፥24 ዘፍ3፥6፤ ኤር43፥7
44፥25 ቍ17፤ዘዳ 32፥38፤ምሳ20፥25፤ 31፥10፤ሕዝ20፥39፤ ያዕ 1፥13-15
44፥26 ዘፍ15፥2፤ 22፥16፤ዘዳ32፥40፤ መዝ50፥16፤ኢሳ48፥1 ፤ኤር24፥8፤4፥2፤ሐሥ 19፥13፤ዕብ6፥13-17
44፥27 ዘፍ41፥15፤ ዘሌ26፥38፤ኢዮ15፥ 22፤ኤር1፥12፤9፥16፤ 21፥10፤ዳን9፥14፤አሞ 9፥8፤2ጴጥ3፥9
44፥28 ቍ13-4:17 :25-26፤2ነገ21፥14፤ ኢሳ7፥9፤10፥19፤ኤር 39፥16፤42፥15-18፤45፥5፤ሕዝ6፥8 44፥29 ዘፍ24፥14፤ዘፀ 3፥12፤32፥34፤ዘኍ16፥38፤ምሳ19፥21፤ማቴ12፥38፤24፥3

[ሠ]15 ዕብራይስጡ በግብፅና በጳጥሮስ ይላል::

ይመ)::

44፥15 *ሚስቶቻቸው ... ሴቶች*፤ ቍ.19 ይመ፤ እንዲሁም የቍ.9 ማብ ይመ:: *በሰሜንና በደቡብ (በላዕላይና በታሕታይ) ግብፅ፤* ቍ.1 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ11፥11 ማብ ይመ::

44፥17 *ለሰማይዋ ንግሥት*፤ የ7፥18 ማብ ይመ:: *በመልካም ሁኔታ እንገኝ ነበር*፤ በረጅሙ የምናሴ አገዛዝ ዘመን ይሁዳ አንጻራዊ የሀብት እድገት አሳይታ ነበር::

44፥18 ... *ከተውን ወዲህ* ከ621ዓ.ቅ.ክ እንሥቶ ንጉሡ ኢዮስያስ በጣዖት አምልኮ ክፉኛ የተበከለውን የይሁዳ ሃይማኖት ለማስወገድና እውነተኛው የእግዚአብሔር አምልኮ እቀድሞ ቦታው እንዲመለስ ለማድረግ ከፍተኛ እንቅስቃሴ ያደረገበት ዘመን ነው:: *ሁሉን ነገር አጥተናል*፤ ኢዮስያስ ከሞተ ከ609ዓ.ቅ.ክ እንሥቶ ወረራንና ስደትን ያካተተ ተከታታይ መከራና ጥፋት ይሁዳን ክፉኛ ገጥሞታል:: ሕዝቡ (አባባላቸው ስሕተት መሆኑ ቢታወቅም) መከራው የደረሰባቸው ለሰማይ ንግሥት የሚገባውን አምልኮ ስላልሰጡ መሆኑን ገልጠዋል::

44፥19 *ሴቶቹም፤* "የሰማይ ንግሥት" የሚል መጠሪያ የተሰጣት በባቢሎናውያን ሥርዐተ አምልኮ ከፍተኛ ቦታ የተሰጣት የውበትና የልምላሜ አምላክ ናት፣ ከዚህ የተነሣ ነበር ዋናውን የአምልኮ ስፍራ የያዘችው:: *ባሎቻችን ሳያውቁት ኖሮአልን?* ጠቀሜታ እንዲኖረው ባገባች ሴት የሚፈጸም ሃይማኖታዊ ስእለት (ቍ.25 ይመ):: በባሏ መጽደቅ አለበት (ዘኍ30፥10-15 ይመ):: *እንደ ምስሏ ያለ ዕንጐቻ የጋገርነው*፤ 7፥18 እና ማብ ይመ::

44፥22 *የርግማን ምልክት*፤ ቍ.12 ይመ:: *ሰው የማይኖርበት ባዶ ምድረ በዳ*፤ ቍ.6 ይመ::

44፥23 *ትእዛዙን*፤ እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የገባው ቃል ኪዳን (ዘዳ4፥45፤ 6፥17:22 ይመ)::

44፥25 *እንግዲያውስ ወደ ኋላ አትበሉ*፤ የምፀት አባባል ነው (7፥21 እና ማብ ይመ)::

44፥26 *በታላቁ ስሜ*፤ የ22፥5፤ የዘፍ22፥15 ማብ ይመ:: *ሕያው እግዚአብሔርን!* የዘፍ42፥16 ማብ ይመ::

44፥27 *እተጋባቸዋለሁና*፤ የ1፥12 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 31፥28 ይመ::

44፥28 *በጣም ጥቂት*፤ ቍ.14 ይመ::

ንጉሥ ለናቡከደናፆር አሳልፌ እንደ ሰጠሁ፣ እንዲሁ የግብፅን ንጉሥ ፈርዖን ሖፍራን ሊገ ድሉት ለሚፈልጉ ጠላቶቹ አሳልፌ እሰጠ ዋለሁ።' ”

## ለባሮክ የተነገረ መልእክት

**45** በይሁዳ ንጉሥ በኢዮስያስ ልጅ በኢ ዮአቄም ዘመነ መንግሥት በአራ ተኛው ዓመት፣ ኤርምያስ በቃል የነገረ ውን ባሮክ በብራና ላይ ከጻፈ በኋላ፣ ነቢዩ ኤርምያስ ለኔርያ ልጅ ለባሮክ የተናገረው ይህ ነው፤ [2]“ባሮክ ሆይ፤ የእስራኤል ስምባከ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይል ሃል፤ [3]አንተ፣ ‘*እግዚአብሔር* በሕመሜ ላይ ሐዘን ጨምሮብኛልና ወዮልኝ፤ ከልቅሶዬ ብዛት የተነሣ ደክሜያለሁ፤ ዕረፍትም የለ ኝም’ ብለሃል።”

[4]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “እንዲህ በለው፤ ‘*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በም ድር ሁሉ የገነባሁትን አፈርሳለሁ፤ የተከል ሁትን እነቅላለሁ። [5]ታዲያ፣ ለራስህ ታላቅ ነገር ትሻለህን? በሰው ልጆች ሁሉ ላይ ጥፋት አመጣለሁና አትፈልገው፤ ይላል *እግ ዚአብሔር*፤ ነገር ግን በሄድህበት ሁሉ ሕይወ ትህ እንዲተርፍልህ አደርጋለሁ።' ”

## ስለ ግብፅ የተነገረ መልእክት

**46** ስለ ሕዝቦች ወደ ነቢዩ ወደ ኤርም ያስ የመጣው *የእግዚአብሔር* ቃል ይህ ነው፤

[2]ስለ ግብፅ ፤

በይሁዳ ንጉሥ በኢዮስያስ ልጅ በኢዮአ ቄም ዘመነ መንግሥት በአራተኛው ዓመት በኤፍራጥስ ወንዝ በከርከሚሽ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ባሸነፈው በግብፅ ንጉሥ በፈርዖን ኒካው ሰራዊት ላይ የተነገረ መልእክት ይህ ነው፤

[3]“ትልቁንና ትንሹን ጋሻ አዘጋጁ፤
ለውጊያም ውጡ!
[4]ፈረሶችን ጫኑ፤
በላያቸውም ተቀመጡ፤
የራስ ቍር ደፍታችሁ፣
በየቦታችሁ ቁሙ፤
ጦራችሁን ወልውሉ፤
ጥሩራችሁን ልበሱ!
[5]ነገር ግን ይህ የማየው ምንድነው?
እጅግ ፈርተዋል፤
ወደ ኋላ እያፈገፈጉ ነው፤
ብርቱ ጦረኞቻቸው ተሸንፈዋል፤
ዘወር ብለውም ሳያዩ፣
በፍጥነት እየሸሹ ነው፤
በየቦታውም ሽብር አለ፣”
ይላል *እግዚአብሔር*።
[6]“ፈጣኑ መሸሽ አይችልም፤
ብርቱውም አያመልጥም፤
በሰሜን በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ፣
ተሰናክለው ወደቁ።
[7]“ይህ እንደ ዐባይ ወንዝ ሙላት
የሚዘለው፣
እንደ ደራሽ ወንዝ የሚፈሰው ማነው?
[8]ግብፅ እንደ ዐባይ ወንዝ ሙላት ይዘላል፤
እንደ ደራሽ ወንዝ ይወረወራል፤
‘እወጣለሁ፤ ምድርንም እሸፍናለሁ፤

44፥30 2ነገ25፥1-7፤ኤር24፥8፤25፥19፤43፥9-13፤46፥26፤ሕዝ30፥21፤ 32፥32
45፥1 ዘዐ17፥14፤2ዜና36፥5፤መዝ40፥7፤ኤር32፥12፤51፥59
45፥3 ኢሱ1፥13፤ኢዮ6፥10፤23፥2፤መዝ69፥3፤119፥28፤ኢሳ24፥16፤ማቴ11፥28፤ማር14፥34፤ሮሜ9፥2፤1ቆሮ9፥16፤ዕብ4፥3
45፥4 ዘዳ28፥63፤30፥9፤ኢሳ5፥5-7፤ኤር11፥17፤18፥7-10፤42፥10
45፥5 መዝ68፥20፤131፥1፤ኤር2፥35፤11፥11፤21፥9፤40፥2፤44፥28፤ማቴ6፥25-27:33
46፥1 ኤር1፥10
46፥2 ዘፍ2፥14፤ዘፀ1፥8፤2ነገ23፥29፤2ዜና35፥20፤ኤር1፥3፤25፥1፤35፥1፤36፥1፤45፥1፤ዳን 1፥1
46፥3 ኢሳ21፥5
46፥4 1ሳሙ17፥5:38፤2ዜና26፥14፤ነህ4፥16፤ሕዝ21፥9-11
46፥5 ቍ21፤መዝ31፥13፤48፥5፤ኤር48፥44
46፥6 ቍ12:16፤ዘፍ2፥14፤15፥18፤መዝ20፥8፤ኢሳ30፥16
46፥7 ኤር47፥2
46፥8 ሕዝ29፥3:9፤30፥12፤አሞ8፥8፤ዳን11፥10

*44፥30፤ ሖፍራን፤* ከ589-570 ዓ.ቅ.ክ ግብፅን የገዛ ንጉሥ ነው (37፥5 እና ማብ ይመ)። *ሊገድሉት ለሚፈልጉ ጠላቶቹ፤* ሖፍራ የተባለው የገዛ ወገኖቹ ግብፃውያን ሥልጣኑን ለመንጠቅ በተነሡ ጊዜ በተደረገው ትግል ነው። *ሴዴቅያስን … ለናቡከደ ነፆር አሳልፌ እንደ ሰጠሁ፤* 39፥5-7 ይመ።

*45፥1-5፤* ታማኝ ለነበረው ለኤርምያስ ጸሓፊ ለባሮክ የተ ነገረው የሚያጽናና መልእክት ነው (የ32፥12 ማብ ይመ)። ከዘመኑ ቅደም ተከተል ወጣ ያለ ቢመስልም፣ ክፍሉ ከም39-44 ላለው የተመቻቸ ታሪካዊ ጥግሬን በውስጡ አካቶ ይዟል፤ እንዲ ሁም ወደ ም46-51 ላለው ክፍል ጥሩ መሸጋገሪያ ድልድይ ይሆ ናል (የቍ1፤ 46፥2 ማብ ይመ)።

45፥1 *በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት በአራተኛው ዓመት፤* 605 ዓ.ቅ.ክ ነው። የም45 ቅደም ተከተል አቀማመጥ በ36፥8 እና በ36፥9 መካከል ነው (የ36፥8 ማብ ይመ)። *በብራና ላይ ከጻፈ በኋላ፤* 36፥4፤ 36፥2 እና ማብ ይመ።

*45፥3፤* ባሮክ፣ ኤርምያስ ለነቢይነት አገልግሎትና ጥሪ ከተመረጠ በኋላ የደረሰበትን መከራና እስከ ተወሰነ ደረጃ ድረስም የነቢዩ ሐዘን ተካፋይ ነበር (ለምሳሌ 8፥18-9፥2፣ 20፥7-8 ይመ)። *ከልቅሶዬ ብዛት የተነሣ ደክሜያለሁ፤* መዝ6፥6 ይመ። *ዕረፍ ትም የለኝም፤* ሰቆ5፥5 ይመ።

45፥4 *የገነባሁትን አፈርሳለሁ፤ የተከልሁትን እነቅላለሁ፤* የ1፥10 ማብ፤ 2፥21፤ 31፥4-5:28:40፤32፥41፤ 33፥7 ይመ። *በም ድር፤* በቍ5 ያለውን “በሰው ልጆች ሁሉ” የሚለውን፣ 25፥15: 31:46-51 ይመ።

45፥5 *ታላቅ ነገር … አትፈልገው፤* የባሮክ ወንድም ሰራ ያ፣ በሴዴቅያስ መንግሥት ትልቅ ሥልጣን አግኝቷል (32፥12፤ 51፥59 ይመ)፣ ባሮክ ግን ለራሱ ክብር ወይም የራሱን መሻት ለሟሟላት የሚጓጓ መሆን አልነበረበትም። *ሕይወትህ እንዲ ተርፍልህ፤* የ21፥9 ማብ ይመ።

*46፥1-51፥64፤* የ25፥1-38፤25፥13፤25፥19-26 ማብ ይመ። ም46-51 በመንግሥታት ላይ የተነገሩትን ትንቢቶች ያመለክታል (ኢሳ13፥23፤ ሕዝ25-32፤ አሞ1-2፤ ሶፎ2፥4-15 ይመ)። ትንቢ ቶቹ በግብፅ (ም46) ጀምረው፣ በባቢሎን ይጨርሳሉ (ም50-51) ግብፅና ባቢሎን በኤርምያስ የአገልግሎት ዘመን ይሁዳን ለመያዝ ሲፎካከሩ የነበሩ መንግሥታት ናቸው። የትንቢቱ አጠቃላይ ቅን ብር ከምዕራብ ወደ ምሥራቅ አቅጣጫን የተከተለ ነበር።

46፥1 *የእግዚአብሔር ቃል ይህ ነው፤* 14፥1፤ 47፥1፤ 49፥34፤ 50፥1 ይመ። *ሕዝቦች፤* ኤርምያስ ትንቢት እንዲናገር የተጠራባቸው ናቸው (1፥5 እና ማብ ይመ)።

46፥2 *ስለ ግብፅ፤* ኢሳ19፥20፤ ሕዝ29፥32 ይመ። *ኒካው፤* ግብፅን ከ610-597 ዓ.ቅ.ክ የገዛ። *ከርከሚሽ፤* 2ዜና35፥20፤ ኢሳ 10፥9 ይመ። ትርጕሙ የሞዓባውያን ዋና አምላክ የሆነው (2ነገ 23፥13) “የካሞሽ ምሽግ” ማለት ነው፤ ይህም የሚገኘው ኤብላ በሚሰኙት በድንጋይ ላይ ጽሑፎች ነው። *ናቡከደነፆር፤* በጥንቱ ዓለም ታሪክ በከርከሚሽ ጦርነት የግብፅ በባቢሎናውያን መሸነፍ እጅግ ወሳኝ የሆነ ድል ነው፤ ምክንያቱም ግብፅ ለዘመናት ስታልመው የነበረውን፣ በሶርያና በፍልስጥኤም ምድር ኀያል የመሆን ውጥን እንዲያበቃ ያደርጋልና። *በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት በአራተኛው ዓመት፤* 605 ዓ.ቅ.ክ ናቡከደነፆር መግ ዛት የጀመረበት ዓመት ነው (25፥1 ይመ)።

46፥3 *አዘጋጁ፤* ግብፃውያንን ለመሳደብ በምፀት የቀረበ አነጋገር ነው (ለምሳሌ፡- ናሆ2፥1፤3፥14 ይመ)።

46፥4 *ፈረሶችን፤* ግብፅ ምርጥ የሆኑ ፈረሶች መገኛ ነበ ረች (1ነገ10፥28 ይመ)። *ጥሩራችሁን ልበሱ፤* 51፥3 ይመ።

46፥5 *በየቦታውም ሽብር አለ፤* ይህ ሐረግ በ6፥25 ላይ ተጠቅሶአል (የዚያኑ ማብ ይመ)፤ ይህም የተገለጸው ከባቢሎናው ያን ሰራዊት ጋር በተያያዘ መልኩ ነው (6፥22 እና ማብ ይመ)።

46፥7-8 *እንደ ደራሽ ወንዝ የሚፈሰው፤* በሰሜናዊ ግብፅ የአባይ ወንዝ ወደ ተለያዩ አነስተኛ ወንዞች የሚፈስበትን ስፍራ ያመለክታል።

46፥8 *እወጣለሁ፤ ምድርንም እሸፍናለሁ፤* ስለ አሶርም

ከተሞችንና ነዋሪዎቻቸውን
አጠፋለሁ’ ይላል።

[9]ፈረሶች ሆይ ዘላችሁ ውጡ!
ሠረገሎችም ሽምጥጡ፤
ጋሻ ያነገባችሁ የኢትዮጵያና*
የፉጥ ሰዎች፣
ቀስት የገተራችሁ የሉድ ጀግኖች፣
እናንተ ብርቱ ጦረኞች ተነሥታችሁ
ዝመቱ።

[10]ያ ቀን ግን የሰራዊት ጌታ የእግዚአ
ብሔር ቀን ነው፤
ጠላቶቹን የሚበቀልበት የበቀል ቀን።
ሰይፍ እስኪጠግብ ድረስ ይበላል፤
ጥማቱም እስኪረካ ድረስ ደም
ይጠጣል።
በሰሜን ምድር በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ፣
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር መሥዋዕት
አዘጋጅቶአልና።

[11]“ድንግሊቱ የግብፅ ሴት ልጅ ሆይ፤
ወደ ገለዓድ ውጪ፤ የሚቀባ
መድኀኒትም አምጪ፤
ነገር ግን መድኀኒት የምታበዢው በከንቱ
ነው፤
ፈውስ አታገኚም።

[12]ሕዝቦች ኀፍረትሽን ይሰማሉ፤
ልቅሶሽም ምድርን ይሞላል።
ጦረኛ በጦረኛው ይደናቀፋል፤
ሁለቱም ተያይዘው ይወድቃሉ።”

[13]የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደናፆር መጥቶ ግብፅን እንደሚወጋ፣ እግዚአብሔር ለነቢዩ ለኤርምያስ የተናገረው መልእክት ይህ ነው፤

[14]“ይህን በግብፅ ተናገር፤ በሚግዶልም
አሰማ፤
በሜምፊስና* በጣፍናስም እንዲህ ብለህ
ዐውጅ፤
በቦታችሁ ቁሙ፤ ተዘጋጁም፤
በዙሪያችሁ ያሉትን ሰይፍ ይበላቸዋልና።

[15]ጦረኞችህ ለምን ተዘረሩ?
እግዚአብሔር ገፍትሮ ስለሚጥላቸው
መቆም አይችሉም።

[16]ደጋግመው ይሰናከላሉ፣
አንዱም በሌላው ላይ ይወድቃል፤
‘ተነሡ እንሂድ፤
ወደ ሕዝባችንና ወደ ትውልድ
አገራችን እንመለስ፤
ከጠላትም ሰይፍ እናምልጥ’ ይላሉ።

[17]በዚያም የግብፅን ንጉሥ ፈርዖንን፣
በተሰጠው ዕድል ያልተጠቀመ፣
አለሁ አለሁ ባይ ደንፊ!’ ብለው
ይጠሩታል።

[18]ስሙ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
የሆነው ንጉሡ እንዲህ ይላል፤
በሕያውነቴ እምላለሁ።
በተራሮች መካከል ያለውን የታቦር ተራራ
የሚመስል፣
ባሕርም አጠገብ ያለውን የቀርሜሎስ
ተራራ የሚመስል አንድ የሚመጣ
አለ።

[19]እናንተ በግብፅ የምትኖሩ ሆይ፤
በምርኮ ለመወሰድ ጓዛችሁን አሰናዱ፤
ሜምፎስ ፈራርሳ፣
ሰው የማይኖርባት ባድማ ትሆናለችና።

*9 የላይኛው ዓባይ አካባቢ ነው
*14 ዕብራይስጡ ኖፍ ይላል፤ ቍ19 ይመ።

46፥9 ዘፍ10፥6፤ኢሳ 66፥19፤ኤር47፥3፤ ሕዝ26፥10፤ናሆ3፥2
46፥10 ዘፍ2፥14፤ 15፥18፤ዘሌ3፥9፤ዘኍ 31፥3፤ዘዳ32፥41፤ 2ሳሙ2፥26፤2ነገ23፥ 29-30፤ሕዝ32፥10፡ 42፤ኢል1፥15፤ አብ 1፥15፤ሶፎ1፥7፤2፥12፤
46፥11 ዘፍ37፥25፤ 2ነገ19፥21፤ኤር 30፥13፤ሚክ1፥9
46፥12 ቍ6፤ኢሳ 19፥4፤ናሆ3፥8-10
46፥13 ቍ26፤ኢሳ 19፥1፤ኤር27፥7፤ሕዝ 32፥11
46፥14 ዘዳ32፥42፤ 2ሳሙ2፥26፤ኢሳ19፥ 13፤ኤር24፥8፤43፥8
46፥15 ኢሱ23፥5፤ ኢሳ66፥15-16
46፥16 ቍ6፤ዘሌ 26፥37፤ኢሳ13፥14፤ ኤር 25፥38
46፥17 1ነገ20፥10- 11፤ኢሳ19፥11-16
46፥18 ኢሱ19፥22፤ 1ነገ18፥42፤ኤር 48፥15
46፥19 ኢሳ20፥4፤ 19፥13፤ሕዝ29፥10፡ 12፤35፥7

ተመሳሳይ ተለዋጭ ዘይቤ በኢሳ8፥7-8 ተገልጾአል (የዚያኑ ማብ ይመ)። *ከተሞችንና* ይህ ቃል በዕብራይስጥ የተገለጠው በነጠላ ቍጥር ነው፤ ይሁን እንጂ በዚህ ስፍራና በ8፥16 በብዙ ቍጥር ተጠቅሶአል።

46፥9 *ዘላችሁ ውጡ፤* የቍ3 ማብ ይመ፤ 8፥6፤ ናሆ3፥3 ይመ። *ሠረገሎችም ሽምጥጡ፤* ናሆ2፥4 ይመ። *የፉጥ፤* የዘፍ10፥6 ማብ ይመ። *የሉድ፤* የኢሳ66፥19 ማብ ይመ። ከኢትዮጵያ፣ ከፉጥና ከሉድ የመጡ ሰዎች በግብፅ ሰራዊት ውስጥ ቅጥረኛ ወታደሮች ናቸው።

46፥10 *የበቀል ቀን፤* ኢሳ34፥8 እና ማብ ይመ። እግዚአብሔር ግብፅ በይሁዳ ላይ የፈጸመችውን ጭካኔ ይበቀላል (ለምሳሌ 2ነገ28፥29፡33-35 ይመ)። *ሰይፍ ... ይበላል፤* ቍ14 ይመ። *ጥማቱም እስኪረካ ድረስ ደም ይጠጣል ... መሥዋዕት አዘጋጅቶአልና፤* አብዛኛውን ጊዜ ጦርነት መሥዋዕት ከማቅረብ ጋር ተነጻጽሮአል (ኢሳ34፥5-7 እና ማብ፤ ሶፎ1፥7-8 ይመ)።

46፥11 *ገለዓድ ... የሚቀባ መድኃኒት፤* 8፥22 እና ማብ ይመ። *ድንግሊቱ የግብፅ ሴት ልጅ ሆይ፤* ቍ19፤ ኢሳ23፥12 እና ማብ፤ ኢሳ47፥14-17 እና ማብ፤ 18፥13፤ 31፥4:21 ይመ። *መድኀኒት የምታበዢው በከንቱ ነው፤ ፈውስ አታገኚም፤* በሕክምና ሙያ ታላቅ እድገት ከነበራት ከግብፅ ጋር ሲነጻጸር ምፀት ነው።

46፥12 *ይደናቀፋል ... ይወድቃሉ፤* ቍ6፥16 ይመ።

46፥13 *ናቡከደነፆር ... ግብፅን እንደሚወጋ፤* ከከርከሚሽ ጦርነት በኋላ (ቍ2 ላይ ያለውን ማብ ይመ)፣ በ568-567 ዓ.ቅ.ክ ነው።

46፥14 *በሚግዶልም፤* የ44፥1 ማብ ይመ። *በሜምፎስና በጣፍናስም፤* 44፥1፤ የ2፥16 ማብ፤ ኢሳ19፥13 ይመ። *በቦታችሁ ቁሙ፤* ቍ4 ይመ። *ሰይፍ ይበላቸዋልና፤* ቍ10 ይመ።

46፥15 *ጦረኞችህ፤* ይህን ቃል የሚተካው የዕብራይስጥ ቃል፣ በቍ5፡9፡12 “ጦረኛ” ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ አይደለም፤ ቃል በቃል ከታየ፣ “ብርቱዎች” ማለት ሲሆን አብዛኛውን ጊዜ ኀይለኛ እንስሳትን የሚያመለክት ነው (8፥16፤ 50፥11፤ 47፥3፤ መሳ5፥22 ይመ)። በመዝ22፥12፤ 50፥13፤ 68፥30፤ ኢሳ 34፥7 የዕብራይስጡ ቃል “በሬዎች” በሚል ተተርጕሟል (የመዝ 68፥30 ማብ ይመ)። *ተዘረሩ፤* የዕብራይስጡ ቃል በሰባ ሊቃናት ትርጕም “አፒስ ሸሸ” ይለዋል። አፒስ በግብፅ በተለይም በሜምፎስ የሚመለክ የበሬ ጣዖት ነው (ቍ14 ይመ)። ስለዚህ የቍ15 ትርጕም አማራጭ ሊሆን የሚችለው፣ “አፒስ” ለምን ፈረጠጠ? በሬህ ለምን መቋቋም አቃተው? “እግዚአብሔር ገፍትሮ ስለ ጣለው አይደለምን?” የሚለው ነው።

46፥16 *ደጋግመው ይሰናከላሉ፤* ቍ6፡12 ይመ። ቃል በቃል ትርጕሙ ሲታይ፣ “ብዙዎችን ያሰናክላል” ነው። *‘ተነሡ እንሂድ፤ ...’ ይላሉ፤* በፈርዖን ሰራዊት ውስጥ ያሉ ቅጥረኛ ወታደሮች (ቍ9 እና ማብ ይመ) ወደ አገራቸው ለመመለስ ይወስናሉ። *ከጠላትም ሰይፍ፤* 25፥38፤ 50፥16 ይመ።

46፥17 *አለሁ አለሁ ባይ ደንፊ፤* በኢሳ30፥7 ግብፅ፣ “ከንቱና ምናምን” ተብላ ተጠርታለች። *በተሰጠው ዕድል ያልተጠቀመ፤* ከከርከሚሽ ጦርነት በኋላ (ቍ2)፣ ናቡከደነፆር የአባቱን ሞት በሰማ ጊዜ ወደ አገሩ ወደ ባቢሎን ተመልሶ ነበር፤ ታዲያ በዚህ ጊዜ ግብፅ ዕድሉን አልተጠቀመችበትም።

46፥18 *በሕያውነቴ እምላለሁ፤* የዘፍ22፥15፤ 42፥16 ማብ ይመ። *ንጉሡ፤* እግዚአብሔር በ8፥19፤ 10፥7፡10፤ 48፥15፤ 51፥57 ንጉሥ ተብሎ ተጠርቷል። *የሚመጣ (እርሱ)፤* ናቡከደነፆርን ነው። *ታቦር ... ቀርሜሎስ፤* በእስራኤል ያሉ ሁለት ትልልቅ ተራሮች ናቸው (የመሳ4፥6፤ መሓ7፥5፤ ኢሳ33፥9 ማብ ይመ)።

46፥19 *በምርኮ ለመወሰድ ጓዛችሁን አሰናዱ፤* በሕዝ12፥3 ላይ ተስተጋብቷል። *በግብፅ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም “የግብፅ ሴት ልጅ” ማለት ነው (ቍ11 እና ማብ ይመ)። *ባድማ*

20“ግብፅ ያማረች ጊደር ናት፣
ነገር ግን ተናዳፊ ዝንብ፣
ከሰሜን ይመጣባታል።
21ቅጥረኞች ወታደሮቿም፣
እንደ ሰቡ ወይፈኖች ናቸው፤
የሚቀጡበት ጊዜ ስለ ደረሰ፣
ጥፋታቸው ስለ ተቃረበ፣
እነርሱም ወደ ኋላ ተመልሰው በአንድነት
ይሸሻሉ፣
በቦታቸውም ጸንተው ሊቋቋሙ
አይችሉም።
22ጠላት ገፍቶ ሲመጣባት፣
ግብፅ እንደሚሸሽ እባብ ታፏጫለች፤
ዛፍ እንደሚቈርጡ ሰዎች፣
መጥረቢያ ይዘው ይመጡባታል።
23ጥቅጥቅ ጫካ ቢሆንም፣ ደን
ይመነጥራሉ፤”
ይላል *እግዚአብሔር*፤
“ብዛታቸው እንደ አንበጣ ነው፤
ሊቈጠሩም አይችሉም።
24የግብፅ ሴት ልጅ ለኀፍረት ትጋለጣለች፤
ለሰሜን ሕዝብም ዐልፋ ትሰጣለች።”

25የእስራኤል አምላክ፣ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “በቴብስ[a] አምላክ በአሞን ላይ፣ በፈርዖን ላይ፣ በግብፅና በአማልክቷ ላይ፣ በነገሥታቷም ላይ፤ እንዲሁም በፈርዖን በሚታመኑት ላይ ቅጣት አመጣለሁ፤ 26ነፍሳቸውን ለሚሹት ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደነፆርና ለጦር መኰንኖቹ አሳልፌ እሰጣቸዋለሁ፤ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ግን ግብፅ እንደ ቀድሞው ዘመን የሰው መኖሪያ ትሆናለች” ይላል *እግዚአብሔር*።

27“አገልጋዬ ያዕቆብ ሆይ፤ አትፍራ፤
እስራኤል ሆይ፤ አትሸበር፤
አንተን ከሩቅ ስፍራ፣
ዘርህንም ተማርኮ ከሄደበት ምድር
አድናለሁ።
ያዕቆብም ተመልሶ በሰላምና በርጋታ
ይቀመጣል፤
የሚያስፈራውም አይኖርም።
28አገልጋዬ ያዕቆብ ሆይ፤ አትፍራ፤
እኔ ከአንተ ጋር ነኝና” ይላል
*እግዚአብሔር*፤
“አንተን የበተንሁበትን ሕዝብ ሁሉ፣
ፈጽሜ ባጠፋም እንኳ፣
አንተን ግን ፈጽሜ አላጠፋህም።
ተገቢውን ቅጣት እሰጥሃለሁ እንጂ፣
ያለ ቅጣት አልተውህም።

## ስለ ፍልስጥኤማውያን የተነገረ መልእክት

47 ፈርዖን ጋዛን ድል ከማድረጉ በፊት፣ ስለ ፍልስጥኤማውያን ወደ ነቢዩ ወደ ኤርምያስ የመጣው የ*እግዚአብሔር* ቃል ይህ ነው፤

2*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

“እነሆ፤ በሰሜን በኩል ውሃ እየሞላ ነው፣
ኀይለኛ ጐርፍ ይሆናል፤
አገሪቷንና በውስጧ ያሉትንም ሁሉ፣
ከተሞቿንና ነዋሪዎቻቸውን ያጥለቀልቃል።
ሕዝቡም ድምፁን ከፍ አድርጎ ይጮኻል፤
የምድሪቱ ነዋሪ ሁሉ ዋይ ዋይ ይላል፤
3ከፈረስ ኰቴ ድምፅ፣
ከጠላት ሠረገላ ጩኸትና፣
ከሠረገላው ሽክርክሪት ፍትጊያ ድምፅ
የተነሣ፣
አባቶች ልጆቻቸውን ለመርዳት ወደ ኋላ
መለስ አይሉም፤
እጃቸውም ስንኩል ይሆናል።
4ፍልስጥኤማውያንን ሁሉ ለማጥፋት፣
ተርፈውም የሚረዷቸውን ሁሉ፣
ከጢሮስና ከሲዶና ለመቍረጥ፣
ቀኑ ደርሶአልና።
*እግዚአብሔር* በከፍቶር[b] ዳርቻ የቀሩትን፣

[a] 25 ወይም ናእ
[b] 4 ቀርጤስ ነው

46፥20 ቍ24፤ኢሳ 14፥31፤ኤር47፥2
46፥21 ቍ5፤2ነገ 7፥6፤ኢዮ18፥20፤ 20፥24፤መዝ18፥18፤ 37፥13፤ኤር18፥17፤ ሉቃ15፥27
46፥22 መዝ74፥5
46፥23 ዘዳ28፥42፤ መሳ7፥12
46፥24 2ነገ24፥7
46፥25 2ነገ24፥7፤ ኢሳ20፥6፤ኤር43፥12 ፤ሕዝ30፥14:22፤ናሆ 3፥8
46፥26 ቍ13፤ኢሳ 19፥4፤ኤር44፥30፤ ሕዝ29፥11-16
46፥27 ኢሳ11፥11፤ 41፥8፤43፥5፤44፥1:2፤ ኤር29፥14፤50፥19፤ 51፥46፤ሚል1፥2
46፥28 ዘፀ14፥22፤ ዘኍ14፥9፤ኢሳ8፥9- 10፤ኤር4፥27
47፥1 ዘፍ10፥14: 19፤መሳ3፥31፤ዘካ 9፥5-7
47፥2 ኢሳ14፥31፤ 15፥3
47፥3 ኢሳ13፥7፤ ኤር46፥9፤50፥43፤ ሕዝ7፥17፤21፥7፤ 23፥24
47፥4 ዘፍ10፥14: 15፤ዘዳ2፥23፤ኢሳ 23፥1፤ኤር25፥22፤ ኢል3፥4፤አሞ1፥9- 10፤ዘካ9፥2-4

*ትሆናለችና*፤ ይሁዳም እንዲሁ በ2፥15፤ 9፥12 ተጠቅሳለች።

46፥20 *ጊደር*፤ ምናልባት የግብፃውያንን የበሬ አምልኮ በምፀት ለማስየት ነው (የቍ15 ማብ ይመ)። *ተናዳፊ ዝንብ*፤ ናቡከደነፆርን ነው፤ አብዛኛውን ጊዜ እንደ ዝንብ፣ አንበጣ ወ.ዘ.ተ … ያሉ ተባዮች ወይም ነፍሳት ወራሪ ጠላትን የሚያመለክቱ ነበሩ (የዘፀ23፥28 ማብ ይመ)።

46፥21 *ቅጥረኞች ወታደሮቿም*፤ የቍ9 ማብ ይመ። *ወይፈኖች*፤ የቍ20 ማብ ይመ። *ጥፋታቸው*፤ 18፥17 ይመ። *የሚቀጡበት ጊዜ ስለ ደረሰ*፤ 11፥23፤ 23፥12፤50፥27 ይመ።

46፥22 *እባብ*፤ አብዛኛውን ጊዜ የግብፅ ፈርዖኖች ኀይለኛነታቸውን ለመግለጽ የሚጠቀሙበት ምልክት ነው (የዘፀ4፥3 ማብ ይመ)። *ጠላት … ዛፍ እንደሚቈርጡ ሰዎች*፤ 21፥14፤ኢሳ 10፥18-19፡33-34 እና ማብ ይመ።

46፥23 *ብዛታቸው እንደ አንበጣ ነው*፤ በዚህ ስፍራ ወራሪው ኀይል እንደ አንበጣ ተቈጥሮአል፤ እንዲሁም በኢል2፥11፡25 አንበጣዎች በወራሪ ኀይል ተመስለዋል።

46፥24 *የግብፅ ሴት ልጅ*፤ የቍ11 ማብ ይመ።

46፥25 *አሞን*፤ በአብዛኛው የግብፅ ታሪክ ውስጥ “አሞን” ዋነኛው የግብፅ አምላክ እንደሆነ ተገልጦአል። እጅግ ክፉ የነበረው የይሁዳ ንጉሥ ምናሴ ልጁን በዚህ የግብፅ ጣዖት ስም ሳይጠራው አልቀረም (2ነገ21፥18፤ 2ዜና33፥22 ይመ)። *በቴብስ*፤ የላይኛው ወይም የደቡባዊ ግብፅ ዋና ከተማ ነው (ሕዝ30፥14-16 ይመ)።

46፥26 *ግብፅ እንደ ቀድሞ ዘመን የሰው መኖሪያ ትሆናለች*፤ ከ48፥47፤ 49፥6፡39 ጋር ያነጻጽሩ። ግብፅ በመሲሑ ዘመን እንደ ገና ትሠራለች (ኢሳ19፥23-25 ይመ)።

46፥27-28፤ ከ30፥10-11 ጀምሮ በአብዛኛው ቃል በቃል የተደገመ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)።

47፥1 *ስለ ፍልስጥኤማውያን*፤ ኢሳ14፥28-32፤ ሕዝ25፥15-17፤ አሞ1፥6-8፤ ሶፎ2፥4-7 ይመ። *ፈርዖን*፤ የተጠቀሰው ለዳግማዊ ኒካው (46፥2፣ የ2ነገ23፥29 ማብ ይመ) ወይም ለሖፍራ ይሁን (የ37፥5፤ 44፥30 ማብ ይመ) የታወቀ ነገር የለም። *ጋዛን*፤ ቍ5፤ 25፥20፤ የመሳ1፥18 ማብ ይመ።

47፥2 *ውሃ እየሞላ ነው*፤ የ46፥7-8 ማብ ይመ። *በሰሜን*፤ በ1፥13-14፤ 46፥20 እንዳለው ባቢሎን። *የምድሪቱ ነዋሪ ሁሉ*፤ ይህ ክፍል በዕብራይስጥ በ8፥16 ላይ ቃል በቃል ተደግሞአል። *የምድሪቱ*፤ ፊንቄና ፍልስጥኤም ናቸው። *ከተሞቿ*፤ የ46፥8 ማብ ይመ፤ ጢሮስንና ሲዶናን (ቍ4ይመ)፤ እንዲሁም ጋዛን፣ አስቀሎናንና (ቍ5ይመ) ሌሎቹን የፍልስጥኤም ከተሞች ያመለክታል።

47፥3 *ኰቴ ድምፅ*፤ ቃል በቃል “ብርቱዎች” ማለት ነው (የ46፥15 ማብ ይመ)። *እጃቸውም ስንኩል ይሆናል*፤ በፍርሀት ሽባ ይሆናሉ ማለት ነው (6፥24፤ ኢሳ13፥7 ይመ)።

47፥4 *ከጢሮስና ከሲዶና*፤ የቍ2፤ 25፥22፤ 27፥3 ማብ ይመ። *ተርፈውም*፤ ቍ5 ይመ። *በከፍቶር*፤ ቀርጤስ (በሶፎ2፥5 ላይ ያለውን ማብ ይመ) በሜድትራኒያን አካባቢ ከሚገኙት ብዙ

ፍልስጥኤማውያንን ሊያጠፋ
ተነሥቶአል።
[5]ጋዛ በማዘን ራሷን ትላጫለች፤
አስቀሎና አፏን ትይዛለች።
በሜዳማ ስፍራ የምትገኙ ትሩፋን ሆይ፤
እስከ መቼ ሰውነታችሁን ትቧጥጣላችሁ?
[6]“ ‘*የእግዚአብሔር* ሰይፍ ሆይ፤
የማታርፈው እስከ መቼ ነው?
ወደ ሰገባህ ተመልሰህ ግባ፤
ጸጥ ብለህ ተቀመጥ’ ትላላችሁ።
[7]ነገር ግን *እግዚአብሔር* አስቀሎናንና
የባሕሩን ዳርቻ፤
እንዲወጋ ሲያዝዘው፤
እንዲፈጽመውም ትእዛዝ ሲሰጠው፤
እንዴት ማረፍ ይችላል?”

## ስለ ሞዓብ የተነገረ መልክት

48፥29-36 ተጓ ምብ-ኢሳ16፥6-12

**48** ስለ ሞዓብ፤
የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ
*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
“ናባው ትጠፋለችና ወዮላት፤
ቂርያታይም ትዋረዳለች፤ ትያዛለችም፤
ምሽጎች[ተ] ይደፈራሉ፤ ይፈራርሳሉም።
[2]ከእንግዲህ ሞዓብ አትከበርም፤
ሰዎች በሐሴቦን[ኀ] ተቀምጠው፤
‘ኑ ያቺን አገር እናጥፋት’ ብለው
ይዶልቱባታል።
መድሜን[ነ] ሆይ፤ አንቺም ደግሞ ጸጥ
ትደረጊያለሽ፤
ሰይፍም ያሳድድሻል።
[3]ከሖሮናይም የሚወጣውን ጩኸት፤
የመውደምና የታላቅ ጥፋት ድምፅ
ስሙ!
[4]ሞዓብ ትሰበራለች፤
ልጆቿም ጩኸት ያሰማሉ።[ኘ]
[5]ከፉኛ እያለቀሱ፤
ወደ ሉሒት ሽቅብ ይወጣሉ፤
ስለ ደረሰባቸውም ጥፋት መራራ ጩኸት
እያሰሙ፤
ወደ ሖርናይም ቍልቍል ይወርዳሉ።
[6]ሽሹ፤ ሕይወታችሁንም አትርፉ!
በምድረ በዳ እንዳለ ቍጥቋጦ[አ] ሁኑ።
[7]በድርጊታችሁና በብልጽግናችሁ
ስለምትታመኑ፤
እናንተም ትማረካላችሁ፤
ካሞሽም ከካህናቱና ከመኳንንቱ ጋር፤
በምርኮ ይወሰዳል።
[8]በእያንዳንዱ ከተማ ላይ አጥፊ ይመጣል፤
አንድም ከተማ አያመልጥም።
*እግዚአብሔር* ተናግሮአልና፤
ሸለቆው ይጠፋል፤
ዐምባውም ይፈርሳል።
[9]በራ እንድታመልጥ፤
ለሞዓብ ክንፍ ስጧት፤
ከተሞቿም ምንም እስከማይኖርባቸው
ድረስ፤
ባድማ[ከ] ይሆናሉ።
[10]“*የእግዚአብሔርን* ሥራ በቸልታ
የሚያከናውን ርጉም ይሁን፤
ሰይፉን ደም ከማፍሰስ የሚከላከል

47፥5 ዘሌ19፥28፤ ኤር25፥20፤41፥5
47፥6 ኢሳ34፥5፤ ኤር12፥12፤48፥10፤ 50፥35፤ሕዝ21፥30
47፥7 ሕዝ25፥15-17
48፥1 ዘፍ19፥37፤ ዘኍ32፥37፡38፤ዘዳ 23፥6፤ኢሱ 3፥19
48፥2 ቍ42፤ዘኍ 21፥25፤ኢሱ13፥26፤ ኢሳ16፥14
48፥3 ኢሳ15፥5
48፥5 ቍ3፤ኢሳ 15፥5
48፥6 ዘፍ19፥17፤ ኤር 17፥6
48፥7 ዘኍ21፥29፤ መዝ49፥6፤ምሳ11፥28 ፤ኢሳ46፥1-2፤ኤር 49፥3፤አሞ 2፥3
48፥8 ዘፀ12፥23፤ ኢሱ13፥9፤ኤር 4፥7
48፥9 መሳ9፥45፤ ኤር51፥29
48፥10 ሳሙ-15፥11 ፤1ነገ20፥42፤2ነገ 13፥15-19፤ኤር47፥6

[ተ]1 ወይም *ሚሥጋብ*
[ኀ]2 *ሐሴቦን* የሚለው የዕብራይስጡ ቃል አነባበብ *መዶለት* ከሚለው የዕብራይስጥ ቃል ጋር ተመሳሳይ ነው።
[ነ]2 *መድሜን* የሚለው የሞአባውያን ከተማ ስም አነባበብ *ጸጥ* ከሚለው የዕብራይስጥ ቃል ጋር ተመሳሳይ ነው።
[ኘ]4 የዕብራይስጡና የሰብዓ ሊቃናት ትርጒሞች *ለዞአር ያውጃሉ* ይላሉ
[አ]6 ወይም *እንደ አሮኤር*
[ከ]9 ወይም *የተተወች ምድር እንድትሆን/ በሞዓብ ላይ ጨው ነስንሱባት*

ደሴቶች አንዱ የፍልስጥኤም መኖሪያ እንደ ሆነ ይገመታል (ዘፍ10፥4 እና ማብ፤ ዘዳ2፥23 ይመ)።

47፥5 *ጋዛ፤* ቍ1፤ 25፥20፤ የመሳ1፥18 ማብ ይመ። *በማዘን ራሷን ትላጫለች፤* የ16፥6 ማብ፤ 48፥37 ይመ። አስቀሎና፤ ቍ7፤ 25፥20፤ የመሳ1፥18 ማብ ይመ። *አፏን ትይዛለች፤* የሐዘን ምልክት ነው (ሰቆ2፥10)። *ትሩፋን፤* የቍ4 ማብ ይመ። *በሜዳማ ስፍራ፤* ከይሁዳ የፍልስጥኤምን ምድር ከሚለየው የተራራ ግርጌ በስተ ምዕራብ ያለው ከዘመናዊው ጋዛ ምድር የሚተካከል ስፍራ ነው። *ሰውነታችሁን ትቧጥጣላችሁ፤* የ16፥6 ማብ 48፥37 ይመ።

47፥6 *ተመልሰህ (አንተ)፤* ፍልስጥኤማውያንን ነው።

47፥7 *አስቀሎናንና ... እንዲወጋ፤* ይህ የተፈጸመው ናቡከደነፆር በ604 ዓ.ቅ.ክ ላይ ይህን ስፍራ በያዘ ጊዜ ነበር። *የባሕሩን ዳርቻ፤* ሕዝ25፥16 ይመ፤ የፍልስጥኤምን ረባዳ ምድር ለማለት ነው (የቍ5 ማብ ይመ)።

48፥1 *ስለ ሞዓብ፤* ኢሳ15-16፤ ሕዝ25፥8-11፤ አሞ2፥1-3፤ ሶፎ2፥8-11 ይመ። አይሁዳዊው የታሪክ ጸሓፊ፤ ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን (ጆሴፈስ) ሞአብ እንደምትጠፋ ኤርምያስ አስቀድሞ የተናገረው ትንቢት “ናቡከደነፆር በነገሠ በሃያ ሦስተኛው ዓመት” (582 ዓ.ቅ.ክ ማለት ነው፤ 52፥34 ይመ) በትክክል መፈጸሙን የጥንቱ ታሪክ (አንቲኪይቲ) በተባለው መጽሐፉ በ10፡9፡7 ላይ ገልጾታል። *ናባው፤* ቍ22 ይመ። ቀድሞ ለሮብዓም ነገድ በዕጣ የተደለደለች ከተማ ናት (ዘኍ32፥3፡37-38 ይመ። እንዲሁም ኢሳ 15፥2 እና ማብ ይመ)። *ቂርያታይም፤* ቍ23 ይመ። የጥንት ከተማ ናት (ዘፍ14፥5 ይመ)፤ ይህችም መጀመሪያ ለሮብዓም ነገድ በዕጣ የተደለደለች ናት (ኢያ13፥19 እና ማብ ይመ)። ናባው፤ ቂርያታይምና በዚህ መጽሐፍ የተጠቀሱት ሌሎች ጥቂት ከተሞች የሞዓብ ንጉሥ ሜሻ ባስቀረጸው በአንድ በታወቀ የድንጋይ ላይ ጽሑፍ ስማቸው ተጠቅሶአል (2ነገ3፥4 ይመ)፤ ይህም ጽሑፍ በ1868 ዓ.ም ተገኝቷል።

48፥2 *ሐሴቦን፤* ቍ34፡45፤ 49፥3፤ ዘኍ21፥25 ይመ። ቀድሞ ለሮብዓም ነገድ የተደለደለች ከተማ ነበረች (ዘኍ32፥37፤ ኢያ13፥17 ይመ)፤ በኋላ ግን የሌዋውያን ከተማ ሆና ለጋድ ተሰጥታለች (ኢያ21፥39 ይመ)። *ይዶልቱባታል፤* ቃሉ በዕብራይስጥ ሁለት ትርጒም የሚሰጥ ስለሆነ ሐሴቦን ከሚለውም ቃል ጋር ግንኙነት አለው።

48፥3 *ሖሮናይም፤* ቍ5፡34 ይመ። የምትገኝበት ትክክለኛ ቦታ በውል አይታወቅም።

48፥4 *ትሰበራለች፤* እንደ ሸክላ ዕቃ ማለት ነው (19፥11 ይመ)።

48፥5 *ሉሒት፤* ያለችበት ቦታ በትክክል አይታወቅም (ኢሳ 15፥5 ይመ)።

48፥6 *ሽሹ፤* ሕይወታችሁን ለማትረፍ ፈጥናችሁ ውጡ። 51፥6 ይመ። *እንዳለ ቍጥቋጦ፤* የ17፥6 ማብ ይመ።

48፥7 *ካሞሽም፤* ቍ13፡46 ይመ፤ ካሞሽ የሞዓብ አገር ዋነኛ ጣዖት ነው (1ነገ11፥7፡33፤ 2ነገ23፥13 ይመ)። ... *በምርኮ ይወሰዳል፤* የተለመደ አባባልን የያዘ ሐረግ (49፥3፤ አሞ 1፥15 ይመ)። አሕዛብ ለአማልክታቸው የሠሯቸውን የጣዖታት ምስሎች ከቦታ ቦታ ተሸክሞ ማዘዋወር የተለመደ ነበር (43፥12፤ አሞ 5፥26 ይመ)።

48፥8 *አጥፊ፤* ቍ32 ይመ። ናቡከደነፆር ሊሆን ይችላል። *ሸለቆው ... ዐምባውም፤* ከአብዛኛው የሞዓብ ምዕራቡ ክፍል ላይ ለቆመ ሰው የዮርዳኖስ ሸለቆ ፍንትው ብሎ ይታየዋል።

48፥10 *በቸልታ፤* ወይም “በሽንፈት” (ይህም በምሳ10፥4፤ 12፥24 ላይ ተጽፎ እንደምናገኘው ዐይነት ማለት ነው። ሞዓብን እንዲያጠፉ እግዚአብሔር ያዘዛቸው ወገኖች እንደ ታዘዙት እን ዲያደርጉ ወይም ማድረግ ያለባቸው መሆኑን ተረድተው በአስ

የተረገመ ይሁን፤

[11]"ሞዓብ በአምቡላው ላይ እንዳረፈ
የወይን ጠጅ፣
ከልጅነት ጀምሮ የተረጋጋ ነበረ፤
ከዕቃ ወደ ዕቃ አልተገላበጠም፤
በምርኮም አልተወሰደም፤
ቃናው እንዳለ ነው፤
መዐዛውም አልተለወጠም።
[12]ስለዚህ ዕቃውን የሚገለብጡ ሰዎችን፤
የምልክበት ጊዜ ይመጣል፤"
ይላል እግዚአብሔር።
"እነርሱም ይደፉታል፤
ዕቃውን ባዶ ያስቀራሉ፤
ማንቆርቆሪያዎቹንም ይሰባብራሉ።
[13]የእስራኤል ቤት፤
በቤቴል ታምኖ እንዳፈረ ሁሉ፣
ሞዓብም በካሞሽ ያፍራል።

[14]"እናንተ፣ 'እኛ ተዋጊዎች ነን፤
በጦርነትም ብርቱ ነን' ልትሉ እንዴት
ቻላችሁ?
[15]ሞዓብ ትጠፋለች፤ ከተሞቿም ይወረራሉ፤
ምርጥ ወጣቶቿም ወደ መታረድ
ይወርዳሉ፤"
ይላል ስሙ የሰራዊት ጌታ
እግዚአብሔር የሆነው ንጉሥ፤
[16]"የሞዓብ ውድቀት ተቃርቦአል፤
ጥፋቱም ፈጥኖ ይመጣበታል።
[17]በዙሪያው የምትኖሩ ሁሉ፤
ዝናውን የምታውቁ ሁሉ አልቅሱለት፤
'ብርቱው ክዘራ፣
የከበረው በትር እንዴት ሊሰበር ቻለ'
በሉ።
[18]"ሞዓብን የሚያጠፋ፣
በአንቺ ላይ ይመጣልና፤
የተመሸጉ ከተሞችሽንም ያጠፋልና፤
አንቺ የዲቦን ሴት ልጅ ሆይ፣
ከክብርሽ ውረጂ፣
በደረቅም መሬት ተቀመጪ።
[19]አንቺ በአሮዔር የምትኖሪ ሆይ፤
በመንገድ አጠገብ ቆመሽ ተመልከቺ፤
የሚሸሸውን ወንድ፣ የምታመልጠውንም
ሴት፣
ምን ተፈጠረ?' ብለሽ ጠይቂ።
[20]ሞዓብ በመፍረሱ ተዋርዷል፤
ዋይ በሉ፤ ጩኹ፤
የሞዓብን መደምሰስ፣
በአርኖን አጠገብ አስታውቁ።
[21]ፍርድ በዐምባው ምድር፦
በሖሎን፣ በያሳና በሜፍዓት ላይ፣
[22]በዲቦን፣ በናባውና በቤት ዲብላታይም
ላይ፣
[23]በቂርያታይም፣ በቤት ጋሙልና
በቤትምዖን ላይ፣
[24]በቂርዮትና በባሶራ ላይ፤
በሩቅና በቅርብ፣
ባሉት በሞዓብ ከተሞች ሁሉ ላይ
መጥቶአል።
[25]የሞዓብ ቀንድ[a] ተቈርጦአል፤
እጁም ተሰባብሮአል፤"
ይላል እግዚአብሔር።

[26]"እግዚአብሔርን ንቆአልና፣
ሞዓብን በመጠጥ አስክሩት።

48፥11 ዘካ1፥15፤ ሶፎ1፥12
48፥13 ቍ7፤ኢሱ 7፥2፤ሆሴ10፥6
48፥14 መዝ33፥16
48፥15 ኢሳ9፥17፤ ኤር46፥18፤51፥40፡57
48፥16 ኢሳ13፥22
48፥17 2ነገ3፥4-5፤ መዝ110፥2
48፥18 ቍ8፤ዘኍ 21፥30፤ኢሱ13፥9፤ ኢሳ47፥1
48፥19 ዘኍ32፥34
48፥20 ዘኍ21፥13፤ ኢሳ16፥7
48፥21 ዘኍ21፥23፤ ኢሱ13፥9፡18፡21፤ 15፥51፤ኢሳ15፥4
48፥22 ዘኍ21፥30፤ 32፥38፤ኢሱ 3፥9፡17
48፥23 ዘኍ32፥37፤ ኢሱ13፥17፡19
48፥24 ኢሳ15፥1፤ ኤር49፥13፤አሞ2፥2
48፥25 መዝ10፥15፤ 37፥17፤75፥10፤ሕዝ 30፥21
48፥26 ቍ39፡42፤ 1ሳሙ17፥26፤ኢሳ 28፥8፤ኤር25፥16፡27፤ 51፥39

[a]25 ቀንድ እዚህ ቦታ ኀይልን በትእምርትነት ይመለከታል

ቸኳይ እንዲንቀሳቀሱ የሚገፋፋ ነው።

*48፥11፤* በመጀመሪያዎቹ የክርስትና ዓመታት በአንድ ትልቅ የሸክላ ሰሌዳ ላይ በዕብራይስጥ ቋንቋ የተቀረጸ የዚህ ቍጥር ቅጂ (ማኅተም) ተገኝቶአል፤ ማኅተሙም የወይን ጠጅ ገንቦዎች ተሞልተው በቅጥራን በሚከደኑበትና በሚታሸጉበት ጊዜ፣ የሚታተሙበት እንደ ነበር ግልጽ ነው። *ከልጅነት ጀምሮ፤* ከመጀመሪያ ታሪኳ አንሥቶ። *እንዳረፈ የወይን ጠጅ፤* ሞዓብ በወይን ተክሎቿ እጅግ የታወቀች ስለ ነበረች፣ ያን ለማሳየት የገባ ሐረግ (ቍ32-33፤ ኢሳ16፥8-10 ይመ)። *በአምቡላው ላይ እንዳረፈ፤* እንዲብላላ ተፈልጎ ማለት ነው (ኢሳ25፥6 ይመ)። *በምርኮም አልተወሰደም፤* እንደ እስራኤል ማለት ነው።

48፥12 *ጊዜ ይመጣል፤* ሞዓብ የምትጠፋበት (የቍ1 ማብ ይመ)። *ከዕቃ ወደ ዕቃ አልተገላበጠም፤* ከሥር ያለው ዝቃጭ እዚያው እንዳለ እንዲቀር ዝቅ ብለው ከላይ ያለውን እያጠለሉ መቅዳታቸውን ለማሳየት ነው። ይሁን እንጂ እነዚህ ሰዎች የእግዚአብሔርን የፍርድ ቅጣት ለመፈጸም የተመደቡ ስለ ሆነ ሞዓብን "ይሰብራሉ" (ቍ4 እና ማብ ይመ)።

48፥13 *በካሞሽ፤* የቍ7 ማብ ይመ። *የእስራኤል ቤት፤* ሰሜኑ የእስራኤል መንግሥት፤ ይህ መንግሥት በ722-721 ዓ.ቅ.ክ ላይ ተደምስሶና ሕዝቡም በምርኮ ተወስዶአል። *በቤቴል፤* ከኢዮርብዓም የወርቅ ጥጃዎች አንዱ የቆመበት ታዋቂ ከተማ (1ነገ 12፥28-30) አልያም በዚያ ዘመን ከተቀረጸው ከባቢሎናውያን ዐለት ላይ በተቀረጸው ሰሌዳ፣ እንዲሁም ከመቶ ዓመት በኋላ በኤሌፋንታይን "የሸንበቆ ልባስ" ላይ ተጽፎ በተገኘው መግለጫ መሠረት እንዲታወቀው ከካሞሽ ፓፒረስ ጋር በተጓዳኝ የሚጠራው የምዕራቡ ሴማዊ ክፍል ጣዖተ አምላክ ሊሆን ይችላል።

48፥14 *ልትሉ እንዴት ቻላችሁ?* 2፥23፤ 8፥8 ይመ።

48፥15 *ወደ መታረድ ይወርዳሉ፤* 50፥27 ይመ። የጦርነት ዕልቂት ለመሥዋዕት ከሚቀርብ እንስሳ ጋር ተመስሎ ትዝቢት ስለ መነገሩ ኢሳ34፥6 እና ማብ ይመ። *ንጉሥ፤* የ46፥18 ማብ ይመ። እውነተኛው ንጉሥ እግዚአብሔር እንጂ ካሞሽ አይደለም።

*48፥16፤* ዘፀ32፥35 ይመ።

48፥17 *በዙሪያው የምትኖሩ ... ዝናውን የምታውቁ፤* በቅርብም በሩቅም ያሉ መንግሥታት። *ብርቱው፤* በአንድ ወቅት ሞዓብ ኀያልና ይፈራ የነበረበት ጊዜ ነበር 927፥3፤ 2ነገ1፥1፤ 3፥5፤ 24፥2 ይመ)። *ከዘራ የከበረው በትር፤* የሥልጣንና የአገዛዝ ምልክት (ዘፍ49፥10፤ መዝ2፥9፤ ሕዝ19፥11፡14 ይመ)።

48፥18 ... *ውረጂ* ... *ተቀመጪ፤* ኢሳ47፥1 እና ማብ ይመ። *የ ... ሴት ልጅ፤* የኢሳ23፥10 ማብ ይመ። *ዲቦን፤* ቍ22፤ ዘኍ21፥30 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ15፥2 ይመ።

48፥19 *በአሮዔር፤* ዘኍ32፥34፤ ዘዳ2፥36 ይመ።

48፥20 *በአርኖን፤* በሞዓብ የሚገኝ ታላቅ ወንዝ።

48፥21 *በዐምባው ምድር፤* የቍ8 ማብ ይመ። *በሖሎን፤* በኢያሱ 15፥21፤ 21፥15 ላይ የተጠቀሰችው ከተማ አይደለችም። ያለችበት ቦታ የት እንደ ሆነም አይታወቅም። *በያሳና፤* 1ዜና 6፥78 ይመ። ያሐድ ተብላም ትጠራለች (ቍ34 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ 15፥4 እና ማብ ይመ)።

48፥22 *በዲቦን፤* ቍ18 ይመ። *በናባውና፤* ቍ1 ይመ። *በቤት ዲብላታይም፤* ምናልባት ከአልሞን ዲብላታይም ጋር አንድ ሊሆን ይችላል። ዘኍ33፥46 ይመ።

48፥23 *በቂርያታይም፤* የቍ1 ማብ ይመ። *በቤት ጋሙልና፤* ባሁኑ ጊዜ ቂርያት ገውሜል ትባላለች። የምትገኘውም ከአሮኤር በስተ ምሥራቅ 8 ኪሎ ሜትር ርቃ ነው። *በቤትምዖን፤* ከበአል ሜአን ጋር አንድ ናት (ዘኍ32፥38 ይመ)፤ እንዲሁም ቤትባአል ሚኦን (ኢያ13፥17 ይመ)።

48፥24 *በቂርዮትና፤* አሞ2፥2 ይመ። የነበረችበት ቦታ በትክክል ተለይቶ አይታወቅም። *በባሶራ፤* በኤዶም የምትገኘው ቦስራ አይደለችም (49፥13፡22 ይመ)፤ የቤዜር ሌላው ስሟ ሲሆን፣ የምትገኘውም በሞዓብ ምድር ነው (የዘዳ4፥43 ማብ ይመ)።

*48፥26፤* እግዚአብሔር ለባቢሎናውያን ወራሪዎች የተናገረው ነው። *በመጠጥ አስክሩት፤* የእግዚአብሔርን የቍጣውን ጽዋ

ሞዓብ በትፋቱ ላይ ይንከባለል፤
ለመዘባበቻም ይሁን።
[27]በእስራኤል ላይ ስታላግጥ አልነበረምን?
ስለ እርሷ በተናገርህ ቍጥር፣
እያቃለልሃት ራስህን የምትነቀንቀውስ፣
ከሌቦች ጋር ስትሰርቅ ተይዛለችን?
[28]እናንተ በሞዓብ የምትኖሩ ሆይ፤
ከከተማ ወጥታችሁ በዐለት መካከል
ኑሩ፤
በገደል አፋፍ ላይ ጐጆዋን
እንደምትሠራ፣
እንደ ርግብ ሁኑ።
[29]"ስለ ሞዓብ ትዕቢት፣
ስለ እብሪቱና ስለ ኵራቱ፣
ስለ ትምክሕቱና ስለ መጓደዱ፣
ስለ ልቡም ማበጥ ሰምተናል።
[30]መዳፉን ዐውቃለሁ፤ ነገር ግን ከንቱ
ነው፤"
ይላል እግዚአብሔር።
"ጕራውም ፋይዳ አይኖረውም።
[31]ስለዚህ ለሞዓብ አለቅሳለሁ፤
ለሞዓብ ምድር ሁሉ ዋይ እላለሁ፤
ለቂርሔሬስ ሰዎችም የልቅሶ ድምፅ
አሰማለሁ።
[32]የሴባማ ወይን ሆይ፤
ለኢያዜር ካለቀስሁት እንኳ ይልቅ
አለቅስልሻለሁ፤
ቅርንጫፎችሽ እስከ ባሕሩ ተዘርግተዋል፤
እስከ ኢያዜርም ደርሰዋል፤
ለመከር በደረሰው ፍሬሽና በወይንሽ ላይ፣
አጥፊው መጥቶአል።
[33]ከሞዓብ የአትክልት ቦታና እርሻ፣
ሐሤትና ደስታ ርቆአል፤
የወይን ጠጅ ከመጭመቂያው እንዳይወርድ
አድርቄዋለሁ፤
በእልልታ የሚጨምቀውም አይገኝም፤
በዚያ ድምፅ ቢሰማም፣
የእልልታ ድምፅ አይደለም።
[34]"ከሐሴቦን እስከ ኤልያሊና እስከ ያህጽ፣
ከዞዓር እስከ ሖሮናይም፣ እስከ ዔግላት
ሺሊሺያ ድረስ፣
ጩኸታቸው ከፍ ብሎ ይሰማል፤
የኔሞሬም ውሃ እንኳ ደርቆአልና።

48፥27 ዘዳ28፥37፤ 2ነገ17፥3-6፤ ኢዮ 16፥4፤መዝ44፥14፤ ኤር2፥26፤18፥16፤ ሚክ7፥8-10፤ሶፎ 2፥8፡10
48፥28 ዘኍ8፥8፤ መሳ6፥2፤መሓ 1፥15
48፥29 ዘሌ26፥19፤ ኢዮ40፥12፤መዝ 10፥5፤ምሳ16፥18
48፥30 መዝ10፥3
48፥31 ቍ36፤2ነገ 3፥25፤ኢሳ15፥5-8
48፥32 ዘኍ32፥3፤ ኢያ13፥25
48፥33 ኢሳ24፥7፤ ኢዩ1፥12፤አሞ5፥17
48፥34 ዘኍ13፥10፤ ዘኍ21፥23፡25፤ 32፥3፤ኢያ13፥26፤ ኢሳ15፥4-6
48፥35 ኢሳ15፥2፤ ኤር11፥13
48፥36 ቍ31፤2ነገ 3፥25፤ኢሳ15፥7
48፥37 ዘፍ37፥34፤ ዘሌ19፥27፤2ሳሙ 10፥4፤ኢሳ3፥24፤ 15፥2፤ኤር41፥5፤ 16፥6፤ሕዝ27፥31፤ 29፥18፤አሞ8፥10
48፥38 ኢሳ15፥3፤ ኤር 22፥28
48፥39 ቍ26፤ኤር 50፥23፤
48፥40 ዘዳ28፥49፤ ኢሳ8፥8፤ዕን1፥8
48፥41 ኢሳ15፥1፤ 21፥3፤አሞ2፥16
48፥42 ቍ2፡26፤ ኢሳ16፥14
48፥43 ኢሳ24፥17፤ ኤር49፥5
48፥44 1ነገ19፥7፤ ኢዮ20፥24፤ኢሳ 24፥18፤ኤር11፥23፤ 23፥12፤46፥5

[35]በመስገጃ ኰረብቶች ላይ የሚሠዉትን፣
ለአማልክታቸው የሚያጥኑትን፣
ከሞዓብ አጠፋለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር፤
[36]"ስለዚህ ልቤ ለሞዓብ እንደ ዋሽንት
ያንጐራጕራል፤
ለቂርሔሬስ ሰዎችም እንደ ዋሽንት
ያንጐራጕራል።
ያከማቹት ንብረት ጠፍቶአልና።
[37]የእያንዳንዱ ሰው ራስ፣
ጢምም ሁሉ ተላጭቶአል፤
እጅ ሁሉ ተቸፍችፎአል፤
ወገብም ሁሉ ማቅ ታጥቆአል።
[38]በሞዓብ ቤቶች ጣራ ሁሉ ላይ፤፣
በሕዝብም አደባባዮች፣
ሐዘን እንጂ ሌላ የለም፤
እንደማይፈለግ እንስራ፣
ሞዓብን ሰብሬአለሁና፤"
ይላል እግዚአብሔር።
[39]"እንዴት ተንኰታኰተ! ምንኛስ አለቀሱ!
ሞዓብ እንዴት ዕፍሮ ጀርባውን አዞረ!
ሞዓብ የመሰደቢያ፣
በዙሪያው ላሉትም ሁሉ የሽብር ምልክት
ሆነ።"
[40]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፤ እንደ ንስር ተወርውሮ
ይወርድበታል፤
ክንፎቹንም በሞዓብ ላይ ይዘረጋል።
[41]ከተሞቹ[a] ይወረራሉ፤
ምሽጎቹም ይያዛሉ፤
በዚያን ቀን የሞዓብ ጦረኞች ልብ፣
በምጥ እንደ ተያዘች ሴት ልብ ይሆናል።
[42]ሞዓብ እግዚአብሔርን አቃልሎአልና
ይጠፋል፤
መንግሥትነቱም ይቀራል።
[43]የሞዓብ ሕዝብ ሆይ፤
ሽብርና ጕድጓድ፣ ወጥመድም
ይጠብቅሃል፤"
ይላል እግዚአብሔር።
[44]"ከሽብር የሚሸሽ ሁሉ፣
ጕድጓድ ውስጥ ይገባል፤
ከጕድጓዱም የሚወጣ፣

[a]41 ወይም ቂርያት

ያመለክታል (13፥13፤ 25፥15-17፡28 ይመ)። *በትፋቱም ላይ ይንከባለላል፤* 25፥27፤ ኢሳ19፥14 ይመ። *ለመዘባበቻም ይሁን፤* በአንድ ወቅት ሌሎችን መዘባበቻ እንዳደረጋቸው ቍ27፤ ሶፎ 2፥8፡10 ይመ።

48፥27 *ራስህን የምትነቀንቀውስ፤* 18፥16 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም መዝ64፥8 ይመ።

*48፥28፤ በገደል አፋፍ ... እንደ ርግብ፤* መዝ55፥6-8፤ ማሕ2፥14 ይመ።

*48፥29-30፤* በኢሳ16፥6 ላይ ስለ ሞዓብ የተጻፈውን በስፋት ያቀረበ ክፍል ነው።

48፥29 *ስለ ሞዓብ ትዕቢት፤* ብዙ ጊዜ እንደ ምሳሌ ሆኖ ሲጠቀስ ኖሮአል (ኢሳ25፥10-11፤ ሶፎ2፥8-10 ይመ)።

*48፥31-33፤* ነቢዩ ራሱ (በኢሳ16፥9 ላይ እንደምናገኘው) ነው። ከኢሳ15፥5 ጋርም ያነጻጽሩ።

*48፥34፤* ኢሳ15፥4-6 እና ማብ ይመ።

*48፥36፤* ኢሳ16፥11 ይመ። *ዋሽንት፤* በሥርዐተ ቀብር ላይ ይነፋል (ማቴ9፥23-24 ይመ)።

*48፥37፤* እነዚህ የሐዘን መግለጫ ምልክቶች ናቸው (ኢሳ 15፥2-3 እና ማብ ይመ)። *ተቸፍችፎአል፤* የ16፥6 ማብ ይመ።

48፥38 *እንደማይፈለግ እንስራ ... ሰብሬአለሁና፤* ቍ4 እና የቍ12 ማብ የመ። ስለ ንጉሡ ስለ ኢዮአቄም በ22፥28 ላይ በዝርዝር ከተጻፈው ጋር ያነጻጽሩ (የዚያኑ ማብ ይመ)።

48፥39 *የመሰደቢያ፤* ቍ26 እና ማብ ይመ።

*48፥40-41፤* ኤዶምን በተመለከተ በ49፥22 ላይ የተጻፈው እዚህ ላይ ተስተጋብቷል።

48፥40 *ንስር፤* ናቡከደነፆርን ያመለክታል (በሕዝ17፥3 ላይ እንደ ተጻፈው ማለት ነው)፤ ዘዳ28፥49 እና ማብ ይመ።

48፥41 *ከተሞቹ፤* የትኞቹ እንደ ሆኑ በውል ተለይተው አይታወቁም (ቍ24 ይመ፤ እንዲሁም የአሞ2፥2 ማብ ይመ)።

48፥43 *ሽብርና ጕድጓድ ወጥመድም፤* የጥንቱ የዕብራይስጥ ቅጅ ኤርምያስ ይህን ሐረግ ይወደው እንደ ነበር በሚገባ ያሳያል።

48፥44 *የሚሸሽ ... ይገባል ... የሚወጣ ... ይያዛል፤*

በወጥመድ ይያዛል፤
በሞዓብ ላይ፣
የቅጣቱን ዓመት አመጣለሁና፣”
ይላል እግዚአብሔር፤

[45]“የሞዓብን ግንባር፣
የደንፊዎችን ዐናት የሚያቃጥል፣
እሳት ከሐሴቦን፣
ነበልባል ከሴዎን ቤት ወጥቶአልና፤
ኰብላዮች በሐሴቦን ጥላ ሥር፣
ተስፋ ቈርጠው ቆመዋል::
[46]ሞዓብ ሆይ፤ ወዮልህ!
የካሞሽ ሕዝብ ተደምስሶአል፤
ወንዶች ልጆችህ በምርኮ ተወስደዋል፣
ሴቶች ልጆችህም ተግዘዋል::
[47]“ነገር ግን የኋላ ኋላ፣
የሞዓብን ምርኮ እመልሳለሁ፤”
ይላል እግዚአብሔር::
በሞዓብ ላይ የተወሰነው ፍርድ
ይኸው ነው::

## ስለ አሞን የተነገረ መልእክት

**49** ስለ አሞናውያን፤
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“እስራኤል ወንዶች ልጆች አልወለደምን?
ወራሾችስ የሉትምን?
ታዲያ፣ ሚልኮም[1] ጋድን ለምን ወረሰ?
የእርሱ ሰዎች ለምን በከተሞቿ
ይኖራሉ?
[2]ስለዚህ፣ በአሞናውያን ከተማ በረባት
ላይ፣
የጦርነት ውካታ ድምፅ፣
የሚሰማበት ጊዜ ይመጣል፤”
ይላል እግዚአብሔር፤
“እርሷም የፍርስራሽ ክምር ትሆናለች፤
በዙሪያዋ ያሉት መንደሮችም
ይቃጠላሉ፤

48፥45 ዘኍ21፥21፡ 26-28፤24፥17፤ኢሱ 12፥2
48፥46 ዘኍ21፥29
48፥47 መዝ14፥7፤ ኢሳ11፥11፤ኤር 12፥15፤49፥6:39፤ሕዝ 16፥53፤ዳን11፥41
49፥1 ዘፍ19፥38፤ 30፥11፤ዘሌ18፥21፤ 1ሳሙ11፥1-11፤ 2ሳሙ10፥1-19
49፥2 ዘዳ3፥11፤ 13፥16፤ኢሳ14፥2፤ ኤር4፥19፤30፥16፤ ሕዝ21፥28-32፤ 25፥2-11
49፥3 ዘፍ12፥8፤ 37፥34፤ኢሱ8፥28፤ 13፥26፤ኤር48፥7፤ ሶፎ 1፥5
49፥4 ኤር3፥6፤ 9፥23፤21፥13፤1ጢሞ 6፥17
49፥5 ኤር44፥14
49፥6 ኤር12፥14-17፤48፥47
49፥7 ዘፍ25፥30፤ 36፥11:15:34፤መዝ 83፥6
49፥8 ዘፍ10፥7፤ 25፥3፤መሳ6፥2

እስራኤልም ከአገሯ ያስወጧትን፣
ከአገሯ ታስወጣለች፤”
ይላል እግዚአብሔር፤
[3]ሐሴቦን ሆይ፤ ጋይ ጠፍታለችና ዋይ በይ፤
የራባት ሴቶች ልጆች ሆይ ጩኹ፤
ማቅ ለብሳችሁ አልቅሱ፤
ሚልኮም ከካህናቱና ከመኳንንቱ ጋር፣
ተማርኮ ይወሰዳልና፣
በቅጥር ውስጥ ወዲያ ወዲህ ተሯሯጡ::
[4]አንቺ ከዳተኛ ልጅ ሆይ፣
በሸለቆችሽ ለምን ትመኪያለሽ?
ለምንስ በፍሬያማ ሸለቆሽ ትኰራሪያለሽ?
በብልጽግናሽ ተማምነሽ፣
‘ማን ሊነካኝ ይችላል?’ ትያለሽ::
[5]በዙሪያሽ ካሉት ሁሉ ዘንድ፣
ሽብር አመጣብሻለሁ፤”
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤
“እያንዳንዳችሁ ትሰደዳላችሁ፤
በሽሽት ላይ ያሉትንም የሚሰበስብ
አይገኝም::
[6]“ከዚያ በኋላ ግን፣
የአሞናውያንን ምርኮ እመልሳለሁ፣”
ይላል እግዚአብሔር::

## ስለ ኤዶም የተነገረ መልእክት

49፥9-10 ተጓ ምብ-አብ5-6
49፥14-16 ተጓ ምብ-አብ1-4

[7]ስለ ኤዶም፤
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
እንዲህ ይላል፤
“ጥበብ ከቴማን ጠፍቶአልን?
ምክር ከአስተዋዮች ርቆአልን?
ጥበባቸውስ ተሟጧልን?
[8]ዔሳውን በምቀጣ ጊዜ፣
ጥፋት ስለማመጣበት፣

[1] ወይም ንጉሣቸው፤ ዕብራይስጡ መልካም ይላል፤ ቍ3 ይመ::

አንድ ጊዜ ከተወሰነው የእግዚአብሔር ፍርድ በምንም መንገድ ማምለጥ አይቻልም (አሞ5፥19 ይመ)::

*48፥45-46፤* ዘኍ21፥28-29፤ 24፥17ን ያስተጋባል:: በለዓም በሞዓብ ላይ የተናገረው ትንቢት የሚፈጸምበት ጊዜ መቃረቡን የሚገልጽ ነው::

48፥45 *ከሐሴቦን፤* የቍ2 ማብ ይመ:: በግልጽ እንደሚታወቀው በዚህ ጊዜ አገሩን የሚቈጣጠሩት አሞናውያን ነበሩ (49፥3 ይመ):: *ከሴዎን፤* የአሞራውያንን ንጉሥ የሴዎንን ማበር ያመለክታል፤ እስራኤላውያን ከግብፅ በወጡ ጊዜ የንጉሡ መናገሻ ከተማ ሴዎን ነበረች (ዘኍ21፥2 ይመ):: *የደንፊዎችን፤* የቍ29 ማብ ይመ::

48፥46 *የካሞሽ፤* የቍ7 ማብ ይመ::

49፥1 *ስለ አሞናውያን፤* ሕዝ 25፥1-7 ይመ፤ እንዲሁም አሞ1፥13-15፤ ሶፎ2፥8-11 ይመ:: የአሞን ምድር የሚገኘው በዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ፣ ከሞዓብ በስተ ሰሜን ነው (የዘፍ 19፥36-38 ማብ ይመ):: *ሚልኮም፤* የአሞናውያን ዋና የጣዖት አምላክ (1ነገ11፥5:7:33 ይመ):: ሞሎክ ተብሎም ይጠራል:: ሚልኮም ወይም ሞሎክ በምዕራብ ሴማዊ ቋንቋ “ንጉሥ” ከሚለው ቃል ጋር ግንኙነት አለው:: *ጋድን ለምን ወረሰ?* ምናልባትም ዐረፍተ ነገሩ የሚያመለክተው ሣልሳዊ ቴልጌልቴልፌልሶር በ734-732 ዓ.ቅ.ክ ላይ ከዮርዳኖስ ማዶ (ምሥራቅ) ያለውን አገር ከሸነፈ በኋላ ያለውን ሁናቴ ይሆናል:: በኋለኛው ጊዜም አሞናውያን በማንሠራራት ከእስራኤል ነገድ አንዱ በሆነው በጋድ ከተያዘባቸው ግዛት ጥቂቱን ክፍል ወረው ለመያዝ ችለዋል::

49፥2 *የጦርነት ውካታ ድምፅ፤* አሞ1፥14 ይመ:: *በአሞናውያን ከተማ በረባት ላይ፤* የዘዳ3፥11 ማብ ይመ:: *ክምር፤* የ30፥18 ማብ ይመ::

49፥3 *ሐሴቦን፤* የ48፥45 ማብ ይመ፤ እንዲሁም መሳ 11፥26-27 ይመ:: *ጋይ፤* በኢሱ8 ላይ የተጠቀሰችው ጋይ አይደለችም፤ ስፍራዋም በውል ተለይቶ አይታወቅም:: *በቅጥር፤* ቃሉ በዕብራይስጥ የአንድን ከተማ ቅጥር የሚያመለክት ሳይሆን፣ አንድ የወይን አትክልት ስፍራን ከሌላው ለመለየት የቆመን ቅጥር የሚያመለክት ነው (ዘኍ21፥24 ይመ):: *ሚልኮም፤* የቍ1 ማብ ይመ:: *ተማርኮ ይወሰዳልና፤* የ48፥7 ማብ ይመ::

49፥4 *አንቺ ከዳተኛ ልጅ ሆይ፤* በ31፥22 ላይ በይሁዳ ሕዝብ ላይ ተነግሮአል:: *በብልጽግናሽ ተማምነሽ፤* በ48፥7 ላይ በሞዓብ ላይ ተነግሮአል:: *ማን ሊነካኝ ይችላል፤* ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን (ጆሲፉስ ፍላብዩስ) የተባለው አይሁዳዊ የታሪክ ጸሓፊ (አንቲኪዩቲስ 10:9:7 በተባለው መጽሐፍ) እንደ ገለጸው የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በነገሠ በ23ኛው ዓመት (በ582 ዓ.ቅ.ክ) ላይ አሞንን አጥፍቷታል::

*49፥6፤* 48፥47 ይመ:: እንዲሁም የ29፥14 ማብ ይመ::

*49፥7-22፤* በዋና ዋና ሐረጎች ጽንሰ ሐሳቦች ከትንቢተ አብድዩ ጋር ተመሳሳይ ነው::

49፥7 *ስለ ኤዶም፤* ኢሳ21፥11-12፤ ዕዝ25፥12-14፤ አሞ 1፥11-12፤አብ1-16 ይመ:: *ጥበብ፤* ኤዶም በዚህ ጕዳይ ጥሩ ስም ነበራት (የኢል1፥1፤ 2፥11 ማብ ይመ):: *ከቴማን፤* ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ የምትገኝ ታዋቂ ከተማ (የኢል2፥11 ማብ ይመ):: በቍ20 ላይ ከኤዶም ጋር ተጓዳኝ ሆና ተጠቅሳለች::

49፥8 *ዔሳውን፤* ከታላላቆቹ አባቶች የአንዱ የያዕቆብ ወንድም፤ ዔሳው፤ ሌላው የኤዶም ስም ነው (ዘፍ32፥28 ይመ):: ዔሳው የያዕቆብ ወንድም የመሆኑ ጕዳይ ኤዶም ለእስራኤል ያለ

እናንተ በድዳን የምትኖሩ ሆይ፤
ወደኋላ ተመልሳችሁ ሽሹ፤ ጥልቅ
ጒድጓድ ውስጥ ተደበቁ።
[9]ወይን ለቃሚዎች ወዳንተ ቢመጡ፣
ጥቂት ወይን አያስቀሩምን?
ሌቦችስ በሌሊት ቢመጡ፣
የሚሰርቁት የሚፈልጉትን ብቻ
አይደለምን?
[10]እኔ ግን ዔሳውን አራቍተዋለሁ፤
መደበቅም እንዳይችል፣
መሸሸጊያ ስፍራዎቹን እገልጣለሁ፤
ልጆቹ፣ ዘመዶቹና ጎረቤቶቹ ይጠፋሉ፤
እርሱም ራሱ አይኖርም።

[11]ወላጆች የሌላቸውን ልጆችህን ተዋቸው፤ እኔ ለሕይወታቸው እጠነቀቃለሁ፤ መበለቶቻችሁም በእኔ ይታመኑ።"

[12]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ከጽዋው መጠጣት የማይገባቸው ሊጠጡ ግድ ከሆነ፣ አንተ እንዴት ሳትቀጣ ትቀራለህ? መቀጣትህ አይቀርም፤ መጠጣት ይገባሃል። [13]ባሶራ ፈራርሳ የድንጋጤ፣ የመዘባበቻና የርግማን ምልክት እንደምትሆን በራሴ ምያለሁ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "ከተሞቿም ሁሉ ለዘላለም ባድማ ይሆናሉ።"

[14]*ከእግዚአብሔር* ዘንድ መልእክት
ሰምቻለሁ፤
"እርሷን ለመውጋት ተሰብሰቡ፤
ለጦርነትም ውጡ!"
የሚል መልእክተኛ ወደ ሕዝቦች
ተልኮአል።
[15]"እነሆ፤ በሕዝቦች መካከል ታናሽ፣
በሰዎችም ዘንድ የተናቅህ አደርግሃለሁ።
[16]አንተ በዐለት ንቃቃት ውስጥ የምትኖር፣
የተራራውንም ከፍታ የያዝህ ሆይ፤
የምትነዛው ሽብር፣
የልብህም ኵራት አታሎሃል፤
መኖሪያህን እንደ ንስር በከፍታ ቦታ
ብትሠራም፣
ከዚያ ወደ ታች እጥልሃለሁ፤"
ይላል *እግዚአብሔር*።
[17]"ኤዶም የድንጋጤ ምልክት ትሆናለች፤
ከቍስሎቿም ሁሉ የተነሣ፣
በዚያ የሚያልፍ ሁሉ በመደነቅ
ያላግጥባታል።"
[18]በዙሪያቸው ካሉት ከተሞች ጋር፣
ሰዶምና ገሞራ እንደ ተገለበጡ፣"
ይላል *እግዚአብሔር*።
እንዲሁ ማንም በዚያ አይኖርም፤
አንድም ሰው አይቀመጥባትም።

[19]"አንበሳ ከዮርዳኖስ ደኖች፣
ወደ ግጦሽ ሜዳ ብቅ እንደሚል፣
እኔም በኤዶም ላይ ድንገት እወጣለሁ፤
ከምድሩም አባርረዋለሁ።
የመረጥሁትን በእርሱ ላይ እሾማለሁ፤
እንደ እኔ ያለ ማን ነው? ማንስ ሊገዳደረኝ
ይችላል?
የትኛውስ እረኛ ሊቋቋመኝ ይችላል?
[20]ስለዚህ *እግዚአብሔር* በኤዶም ላይ
ያለውን ዕቅድ፣
በቴማን በሚኖሩትም ላይ ያሰበውን
አሳብ ስሙ፤
ታናናሹ መንጋ ተጐትቶ ይወሰዳል፤
በእነርሱም ምክንያት መሰማሪያቸውን
ፈጽሞ ያጠፋል።
[21]በውድቀታቸው ድምፅ ምድር
ትናወጣለች፤
ጩኸታቸውም እስከ ቀይ ባሕር+
ያስተጋባል።
[22]እነሆ፤ እንደ ንስር ተወርውሮ
ይወርድባታል፤
ክንፎቹንም በባሶራ ላይ ይዘረጋል፤

49፥10 ዘፍ3፥8፤ኢሳ 34፥10-12፤ኤር11፥23፤ሕዝ35፥4፤አብ 1፥18፤ሚል1፥2-5
49፥11 ዘዳ10፥18፤ ሆሴ14፥3፤ያዕ 1፥27
49፥12 ምሳ11፥31፤ ኢሳ51፥23፤ ኤር 25፥15፤ማቴ20፥22
49፥13 ቍ17፤ዘፍ 22፥16፤36፥33፤ኤር 19፥8፤42፥18፤ሕዝ 35፥9
49፥16 ኢዮ39፥27:28፤ሕዝ35፥13፤አብ 1፥12
49፥17 ቍ13፤ዘዳ 29፥22፤ሕዝ35፥7
49፥18 ቍ33፤ዘፍ 19፥24፤ኢሳ34፥10፤ ኤር23፥14
49፥19 ዘፀ 8፥10፤ 1ሳሙ17፥34:35፤ 2ዜና20፥6፤ኢዮ 9፥19፤ኢሳ46፥5፤ ኤር12፥5፤50፥44
49፥20 ቍ7:10፤ ዘፍ36፥11፤ኢሳ34፥5፤14፥27፤ኤር50፥45፤ አብ1፥10፤ሚል1፥3-4
49፥21 መዝ114፥7፤ኤር50፥46፤51፥29፤ ሕዝ26፥15:18፤ 27፥28፤31፥16
49፥22 ዘፍ36፥33፤ ዘዳ28፥49፤ኢሳ13፥8፤ኤር50፥36፤ሆሴ 8፥1፤ናሆ3፥13፤ዕን 1፥8

+21 ዕብራይስጡ *ያም ሱፍ* ይላል፤ ትርጒሙ የሸንበቆ ባሕር ማለት ነው

ውን ጠላትነት ይበልጥ የከፋ እንዲሆን አድርጎታል (አሞ1፥11፤ አብ10 ይመ)። *ተመልሳችሁ ሽሹ፤* ቍ24፤46፥21 ይመ። *በድዳን፤* 25፥23 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ21፥13፤ የሕዝ25፥13 ማብ ይመ።

*49፥9-10፤* ከአብ5-6 ጋር ተጓዳኝ ነው።

49፥9 *ወይን ለቃሚዎች፤* የቍ13 ማብ ይመ። *ጥቂት ወይን አያስቀሩምን? ቃርሚያውን ለሚቃርሙ ችግረኞች ጥቅም* ሲሉ ነው (የሩት2፥2 ማብ ይመ)።

49፥10 *አራቍተዋለሁ፤* የ13፥22 ማብ ይመ። ... *አይኖርም፤* 31፥15፤ ኢሳ19፥7 ይመ።

*49፥12፤* ከ25፥28-29 የተስተጋባ ሐሳብ ነው። *መጠጣት የማይገባቸው ... እንዴት ሳትቀጣ ትቀራለህ?* ምንም እንኳ በእግዚአብሔር የተመረጡ ቢሆኑም፣ የይሁዳ ሕዝብ በኀጢአታቸው ምክንያት ከመቀጣት አያመልጡም (አሞ3፥2 ይመ)።

49፥13 *በራሴ ምያለሁ፤* የዘፍ22፥16፤ የኢሳ45፥23 ማብ ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ34፥6፤ አሞ1፥12 ማብ ይመ። *ባሶራ፤* በ 48፥24 ላይ የተጠቀሰችው ባሶራ አይደለችም (የዚያኑ ማብ ይመ)። የኤዶም ባሶራ ኤርምያስ በነበረበት ዘመን የኤዶም ዋና ከተማ ሳትሆን አልቀረችም (ቍ22፤ ዘፍ36፥33 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ34፥6፤ አሞ1፥12 ይመ)። በዕብራይስጥ ባሶራ የሚለውን ቃል የሚያስገኘው መነሻ ቃል፣ በቍ9 ላይ ወይን ለቃሚ የሚለውን ቃል ከሚያስገኘው ጋር አንድ ነው። *ፈራርሳ ... የርግማን፤* 25፥15 ይመ። *ለዘላለም ባድማ፤* 25፥9፤ መዝ74፥3፤ ኢሳ 58፥12 እና ማብ ይመ።

*49፥14-16፤* ከአብ1-4 ጋር ተጓዳኝ ነው።

49፥16 *ኵራት፤* በየአቅጣጫው የተያዘበት ኀጢአት (ቍ4፤ አብ11-13 ይመ። ከ48፥29-30 ጋር ያነጻጽሩ)። *በዐለት ንቃቃት፤* በግሪክ "ፔጥራ" ማለት ዐለት ማለት ነው (የ2ነገ14፥7 ማብ ይመ)፤ ኤዶም የምትታወቀው በዚህ ጠንካራ የተራራ ላይ ምሽግ ነው።

*49፥17፤* ከ19፥8 የተስተጋባ ሐሳብ ነው።

*49፥18፤* ከ50፥40 ቃል በቃል የተወሰደና ቍ33ን በከፊል የሚያስተጋባ። *ሰዶምና ገሞራ እንደ ተገለበጡ፤* ዘፍ19፥24-25 ይመ። ከዚያ በኋላ ለደረሱ መከራዎችና ጥፋቶች ዋናው ማነጻጸሪያ በሰዶምና በገሞራ ላይ የደረሰው ጥፋት ነው (የአሞ4፥11 ማብ ይመ)። *በዙሪያቸው ካሉት ከተሞች ጋር፤* የመጀመሪያዎቹ ተጠቃሾች አዳማና ሰቦይም (ዘፍ14፥2:8፤ዘዳ29፥23፤ሆሴ11፥8 ይመ) ናቸው።

*49፥19-21፤* በ50፥44-46 ላይ ስለ ባቢሎን የተነገረው ቃል በቃል እዚህ ላይ ተደግሞአል።

*49፥19፤ ከዮርዳኖስ ደኖች፤* 12፥5 እና ማብ ይመ። *እረኛ፤* ገዥ (የ2፥8 ማብ ይመ)።

49፥20 *በቴማን፤* የቍ7 ማብ ይመ። *መንጋ፤* የኤዶም ሕዝብ።

*49፥22፤* ከ48፥40-41 የተስተጋባ ሐሳብ ነው። *ንስር፤* በ 48፥40 ላይ ናቡከደነፆርን ይተካል (የዚያኑ ማብ ይመ)፤ እዚህም ስፍራ ላይ ናቡከደንፆርን ሊያመለክት ይችላል። ይሁን እንጂ በ 55 ዓ.ቅ.ክ መጀመሪያ ላይ በኤዶማውያን ላይ የታየውን ፍጹም ሽንፈት ያደረሱት የናባጥ ዐረቦች (ምናልባት በሚል 1፥3 ላይ "የምድረ በዳ ቀበሮዎች" የተባሉት ሊሆኑ ይችላሉ) ናቸው። *ባሶራ፤*

በዚያን ቀን የኤዶም ጦረኞች ልብ፣
በምጥ እንደ ተያዘች ሴት ልብ
ይሆናል።

## ስለ ደማስቆ የተነገረ መልእክት

[23]ስለ ደማስቆ፤

“ክፉ ወሬ ሰምተዋልና፣
ሐማትና አርፋድ ደንግጠዋል፣
እንደ[ሀ] ተናወጠ ባሕርም ታውከዋል፤
ልባቸውም ቀልጦአል።
[24]ደማስቆ ተዳከመች፤
ትሸሽም ዘንድ ወደ ኋላ ተመለሰች፤
ብርክ ያዛት፣
ምጥ እንደ ያዛት ሴት፣
ጭንቅና መከራ ዋጣት።
[25]ደስ የምሰኝባት፣
የታወቀችው ከተማ እንዴት ተተወች?
[26]በእርግጥ ወንዶች ወጣቶቿ በየአደባባዩ
ይረግፋሉ፤
በዚያ ቀን ወታደሮቿ ሁሉ
ይወድቃሉ፤”
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤
[27]“በደማስቆ ቅጥር ላይ እሳት እለኩሳለሁ፤
የወልደ አዴርንም ዐምባ ይበላል።”

## ስለ ቄዳርና ስለ ሐጾር የተነገረ መልእክት

[28]የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ስለወጋቸው ስለ ቄዳርና ስለ ሐጾር መንግሥታት የተነገረ፤ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

“ተነሡ፣ ቄዳርን ውጉ፤
የምሥራቅንም ሕዝብ ደምስሱ።
[29]ድንኳኖቻቸውና መንጎቻቸው ይወሰዳሉ፤
መጠለያቸውና ግመሎቻቸው ሳይቀሩ፣
ከነዕቃዎቻቸው ይነጠቃሉ፤
ሰዎች፣ ‘ሽብር በሽብር ላይ
መጥቶባቸዋል፤’
እያሉ ይጮኹባቸዋል።
[30]በሐጾር የምትኖሩ ሆይ፣
በጥድፊያ ሽሹ! በጥልቅ ጕድጓድ
ተሸሸጉ፤”
ይላል እግዚአብሔር፤
የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በእናንተ ላይ
መክሮአልና፣
ወረራም ዶልቶባችኋል።
[31]“ተነሡ፣ ተዘልሎ የተቀመጠውን፣
በራሱ ተማምኖ የሚኖረውን ሕዝብ
ውጉ፤”
ይላል እግዚአብሔር፤
መዝጊያና መቀርቀሪያ በሌለው፤
ለብቻው በሚኖረው ሕዝብ ላይ
ዝመቱ።”
[32]ግመሎቻቸው ይዘረፋሉ፤
ከብቶቻቸውንም እንጋግተው
ይነዱባቸዋል፤
ጠጕሩን የሚቀነብበውን ወገን[+] እበትናለሁ
ከየአቅጣጫው መዓት አመጣባቸዋለሁ፤
ይላል እግዚአብሔር፤
[33]“ሐጾር የቀበሮዎች መፈንጫ፣
ለዘላለም ባድማ ትሆናለች፤
ማንም በዚያ አይኖርም፤
የሚቀመጥባትም አይገኝም።”

## ስለ ኤላም የተነገረ መልእክት

[34]በይሁዳ ንጉሥ በሴዴቅያስ ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ ወደ ነቢዩ ወደ ኤርምያስ የመጣው የእግዚአብሔር ቃል ይህ ነው፤

[35]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

“እነሆ፤ የኀያልነቷን መሠረት፣
የኤላምን ቀስት እሰብራለሁ።
[36]ከአራቱ የሰማይ ማእዘናት፣
በኤላም ላይ አራቱን ነፋሳት አመጣለሁ፤
ወደ አራቱም ነፋሳት እበትናቸዋለሁ፤
ከኤላም የሚማረኩት የማይደርሱበት፣
አገር አይገኝም።
[37]ነፍሳቸውን በሚሹ ጠላቶቻቸው ፊት፣

49፥23 ዘፍ14፥15፤ 49፥4፤1ነገ8፥65፤ 2ነገ14፥28፤18፥34፤ 19፥13፤2ዜና16፥2፤ ኢሳ10፥9፤ሕዝ47፥16 ፤አሞ6፥2፤ዘካ9፥2፤ ሐሥ 9፥2
49፥24 ኤር13፥21
49፥26 ኢሳ9፥17፤ 13፥18፤17፥12-14
49፥27 ዘፍ14፥15፤ 1ነገ15፥18ኤር21፥14 ፤43፥12፤50፥32፤ሕዝ 30፥8፤39፥6፤አሞ 1፥4፤ ኢሳ 17፥1፤
49፥28 ዘፍ25፥13፤ ኢሱ11፥1፤ኤር 10፥22፤መሳ 6፥3
49፥29 ቍ32፤ኤር 6፥25
49፥30 መሳ6፥2፤ ኢሱ11፥1፤ኤር10፥22
49፥31 ሕዝ38፥11
49፥32 ቍ29፡36፤ መሳ6፥5፤ኤር9፥26፤ 13፥24
49፥33 ቍ18፤ኢሱ 11፥1፤ኢሳ13፥22፤ ኤር48፥9፤ 51፥37
49፥34 ዘፍ10፥22፤ 2ነገ 24፥18
49፥35 መዝ37፥15 ፤ኢሳ22፥6
49፥36 ቍ32፤ዳን 11፥4
49፥37 ኤር30፥24፤ 9፥16፤ሕዝ32፥24

[ሀ]23 ዕብራይስጡ *በተናወጠ* ይላል
[+]32 ወይም *በሩቅ ስፍራ ያለውን*

የቍ13 ማብ ይመ።

49፥23 *ስለ ደማስቆ፤* ኢሳ17፤ አሞ1፥3-5 ይመ (እንዲሁም የኢሳ17፥1 ማብ ይመ)። *ሐማትና፤* በአራም ንጉሣዊ ግዛት ውስጥ የታወቀች ከተማ (ኢሳ10፥9 እና ማብ ይመ)። *አርፋድ፣* የኢሳ 10፥9 ማብ ይመ። *እንደ ተናወጠ ባሕርም፤* ኢሳ57፥20 ይመ።

49፥24 *ጭንቅና፤* የ4፥19 ማብ ይመ።

49፥26 በ50፥30 ላይ የተነገረው በዚህም ስፍራ ቃል በቃል ተደግሞአል።

*49፥27፤* ፍርድን በተመለከተ የተለመደ አባባል (የአሞ1፥4 ማብ ይመ)።

49፥28 *ስለ ቄዳርና፤* ኢሳ21፥13-17 ይመ፤ እንዲሁም 2፥10ንና ማብ ይመ። *ሐጾር መንግሥታት፣* ቍ30:33 ይመ። ከገሊላ ባሕር በስተ ሰሜን ያለችው ሐጾር አይደለችም (ኢሱ 11፥1)። እነዚህ መንግሥታት ድዳንን፣ ቴማንን፣ ቡዝን እንዲሁም ሌሎችን የዐረብ ክፍሎች የሚያጠቃልሉ ሊሆኑ ይችላሉ (25፥23-24 እና ማብ ይመ)። ሐጾር የሚለው የተጸውዖ ስም ሥርወ ቃሉ ዐልፎ ዐልፎ “ሰፍራ” ለሚለው የወል ስም የሚገባ መሆኑን ማስተዋል ይገባል። በተለይም ኢሳ42፥11 ይመ፤ እንዲሁም ዘፍ25፥16 ይመ። *ናቡከደነፆር ስለ ወጋቸው፤* በ599-598 ዓ.ቅ.ክ ነው። *የምሥራቅንም ሕዝብ፤* (ኢል1፥3፤ ዕዝ25፥4 ይመ)። በዕብራይስጥ ይህ ቃል “የምሥራቅ ሕዝቦች” ተብሎ ነው ተተርጕሞአል (መሳ6፥3 እና ማብ ይመ)።

49፥29 *ሽብር በሽብር ላይ፤* የ6፥25 ማብ ይመ።

49፥30 *በጥልቅ ጕድጓድ ተሸሸጉ፤* ቍ8 ይመ።

49፥31 *ተዘልሎ፤* ምንም ዐይነት ነገር እንደማይደርስበት በማሰብ (ኢዮ21፥23 ይመ)። *በራሱ ተማምኖ፣* በሰላም ያለ ሥጋት (መሳ18፥7፤ ዕዝ38፥11 ይመ)። *መዝጊያና መቀርቀሪያ፤* ቅጥር በሌላት ከተማ የሚኖሩ ሰዎች (ዘዳ3፥5፤ ይመ። ከኢሳ 23፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። *ለብቻው፣* በአንዳንድ ስፍራዎች የእስራኤልን ሁኔታ ያመለክታል (ዘኍ23፥9፤ ዘዳ33፥28)።

49፥32 *እበትናለሁ፤* ሕዝ5፥12፤ 12፥4 ይመ። *ከየአቅጣጫው መዓት፤* የሰሎሞንን ግዛት በተመለከተ በ1ነገ5፥4 ላይ ከተጻፈው ጋር ያነጻጽሩ።

49፥33 *የቀበሮዎች መፈንጫ፤* የ9፥11 ማብ ይመ። *ማንም በዚያ አይኖርም፣* እዚህ ላይ ቍ18 እንዳለ ተደግሞአል።

49፥34 *ወደ ነቢዩ ወደ ኤርምያስ የመጣው የእግዚአብሔር ቃል ይህ ነው፤* የ46፥1 ማብ ይመ። *ሴዴቅያስ፤* ከ597-586 ዓ.ቅ.ክ ገዝቶአል።

49፥35 *ቀስት፤* የኤላም ሰዎች በቀስት ውጊያ እቻ አልነበራቸውም ኢሳ22፥6 ይመ)።

49፥36 ከኢሳ11፥12 ጋር ያነጻጽሩ። *ወደ አራቱም ነፋሳት እበትናቸዋለሁ፤* በየአቅጣጫው ማለት ነው (ሕዝ37፥9፤ ዳን7፥2፤ 8፥8 ይመ)።

ኤላምን አርበደብዳለሁ፤
በላያቸው ላይ መዓትን፣
ይኸውም ቍጣዬን አመጣባቸዋለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር፤
"ፈጽሜ እስካጠፋቸውም ድረስ፣
በሰይፍ አሳድዳቸዋለሁ።
[38]ዙፋኔን በኤላም እዘረጋለሁ፤
ነገሥታቷንና መኳንንቷን
አጠፋለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር፤
[39]"ነገር ግን የኋላ ኋላ፣
የኤላምን ምርኮ እመልሳለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር።

## ስለ ባቢሎን የተነገረ መልእክት

51፥15-19 ተጓ ምብ-ኤር10፥12-16

**50** እግዚአብሔር ስለ ባቢሎንና ስለ ባቢሎናውያን* ምድር፣ በነቢዩ ኤርምያስ በኩል የተናገረው ቃል ይህ ነው፤
[2]"በሕዝቦች መካከል ተናገሩ፤ አስታውቁም፤
ሰንደቅ ዐላማ አንሡ፣ ዐውጁ፣
አንዳች ሳታስቀሩ፣ እንዲህ በሉ፤
'ባቢሎን ትያዛለች፤
ቤል ይዋረዳል፤
ሜሮዳክ በሽብር ይሞላል፤
ጣዖቶቿ ይዋረዳሉ፤
አማልክቷም ይሸበራሉ።'
[3]ከሰሜን አንድ መንግሥት መጥቶ
ይወጋታል፤
ምድሯንም ባድማ ያደርጋል፤
የሚኖርባትም አይገኝም፤
ሰዎችና እንስሳትም ሸሽተው ይሄዳሉ።
[4]"በዚያ ዘመን፣ በዚያ ጊዜም፤"
ይላል እግዚአብሔር፤
"የእስራኤል ሕዝብና የይሁዳ ሕዝብ
በአንድነት ይመጣሉ፤
ስምባካቸውንም እግዚአብሔርን በመፈለግ
እያለቀሱ ይመጣሉ።
[5]ወደ ጽዮን የሚወስደውን መንገድ
ይጠይቃሉ፤
ፊታቸውንም ወደዚያ ያቀናሉ።
መጥተውም ከቶ በማይረሳ፣
በዘላለም ቃል ኪዳን፣
ከእግዚአብሔር ጋር ይጣበቃሉ።
[6]"ሕዝቤ የጠፉ በጎች ሆነዋል፤
እረኞቻቸው አሳቷቸው፤
በተራሮችም ላይ እንዲቅበዘበዙ
አደረጓቸው፤
በተራራና በኰረብታ ላይ ተንከራተቱ፤
ማደሪያቸውንም ረሱ።
[7]ያገኛቸው ሁሉ ይውጣቸዋል፤
ጠላቶቻቸውም፣ 'እኛ በደለኞች
አይደለንም፤
እነርሱ የአባቶቻቸውን ተስፋ
እግዚአብሔርን፣
እውነተኛ ማደሪያቸው የሆነውን እግዚ
አብሔርን በድለዋል' አሉ።
[8]"ከባቢሎን ሽሹ፤
የባቢሎናውያንን ምድር ልቀቁ፤
መንጋ እንደሚመራ የፍየል አውራ
ሁኑ።
[9]የታላላቅ መንግሥታትን ማኅበር፣
ከሰሜን በባቢሎን ላይ አስነሣለሁ፤
እነርሱም በእርሷ ላይ ይሰለፋሉ፤

49፥39 ኤር48፥47
50፥1 ዘፍ10፥10፤ መዝ137፥8
50፥2 ቍ9፡38፤ ዘሌ26፥30፤ዘዳ30፥4፤ መዝ20፥5፤97፥7፤ኢሳ 13፥2፤21፥9፤46፥1፡6፤ ኤር4፥16፤51፥31፡47፡ 52፤
50፥3 ቍ13፡26፤ ኢሳ14፥22-23፤ 25፥26፤ 41፥25፤ ኤር9፥11፤ሶፎ1፥3
50፥4 ዕዝ3፥12፤ኢሳ 9፥13፤ኤር3፥18፤ሕዝ 37፥17፡22፤ሆሴ3፥5
50፥5 ዘዳ29፥14፤ 1ሳሙ29፥1፤ኢሳ 11፥16፤55፥3፤ኤር 31፥21፤32፥40፤33፥7 ፤ ዕብ8፥6-10
50፥6 ቍ19፤መዝ 95፥10፤119፥176፤ ኤር2፥8፤3፥6፤10፥21፤ 23፥32፤ሕዝ13፥10፤ 34፥6፤ማቴ9፥36፤ 10፥6
50፥7 ኤር2፥3፤ 5፥17፤10፥25፤14፥8፤ ሕዝ35፥12
50፥8 ቍ28፤ኢሳ 48፥20
50፥9 ቍ2፤ኢሳ 13፥17፡18፤ኢሳ41፥ 25፤ኤር25፥14፡26፤

*1 ወይም *ከለዳውያን*፤ በቍ8፡25፡35 እና 45 ይመ።

49፥37 *ፈጽሜ እስካጠፋቸው ... አሳድዳቸዋለሁ*፤ በዕብራይስጥ ይህ ዐረፍተ ነገር በ9፥16 ላይ ቃል በቃል ተደግሞአል።
49፥38 *ዙፋኔን ... እዘረጋለሁ*፤ 1፥15 እና ማብ ይመ።
*49፥39*፤ የ29፥14 ማብ ይመ።
*50፥1-51፥64*፤ ኢሳ13፥1-14፥23፤ 21፥1-9 ይመ። ኤርምያስ ስለ ባቢሎን የተናገረው ትንቢት በሌሎች አሕዛብ ላይ ከተነገረው በጣም ረጅምና (46-51 ምዕራፎች ይመ) ቀደም ሲል በተናገራቸውና አጫጭር በሆኑት ንግሮቹ ላይ ተመሥርቶ እየተስፋፋ የሚሄድ ትንቢት ነው (25፥12-14፡26 ይመ)። የተነገረበት ዘመን ሙሉ በሙሉ ወይም በከፊል 593 ዓ.ቅ.ክ ነው (51፥59 እና ማብ ይመ)። ሁለቱ ምዕራፎች በሦስት ዋና ዋና ክፍሎች ይከፈላሉ (50፥2-28፤ 50፥29-51-26፤ 51፥27-58)፤ እያንዳንዱም ክፍል የይሁዳ ዋነኛ ጠላት በሆነችው ባቢሎን ላይ ለጦርነት በሚያነሣሣ ጥሪ ይጀምራል (50፥2-3፤ 50፥29-32፤ 51፥27-32 ይመ)።
50፥1 *ቃል*፤ በሌላ አባባል "መልእክት" ማለት ነው (በኢሳ46፥13 ላይ እንደ ተጻፈው) ይህም በም50-51 ያለውን አጠቃሉ ይይዛል። *በኩል*፤ 37፥2 ይመ። መልክቱ በመጨረሻ በነቢዩ አማካይነት ለባቢሎን የሚላክ መልእክት ነው። (51፥59-61 ይመ)።
50፥2 *ተናገሩ፤ አስታውቁም*፤ 4፥5፤ 46፥14 ይመ። *ሰንደቅ ዐላማ አንሡ*፤ የኢሳ5፥26 ማብ ይመ። ይህ ሐረግ በ4፥6 ላይ በዕብራይስጥ "ምልክቱን አንሡ" ተብሎ ተተርጕሞአል። *ባቢሎን ትያዛለች*፤ ይህ ትንቢት በ539 ዓ.ቅ.ክ ላይ ተፈጽሞአል። *ቤል*፤ 51፥44፤ ኢሳ46፥1 እና ማብ ይመ። *ይዋረዳል ... በሽብር ይሞላል*፤ የእነዚህ ሐረጎች መደጋገም በአጽንዖት የሚያረጋግጠው፣ የባቢሎንን ዋነኛ አምላክና የምስሉን፣ እንዲሁም የጣዖታትን መጥፋት ነው። *አማልክቷም*፤ የቃሉ ቀጥተኛ ትርጕም "የበግ ወይም የፍየል በጠጥ" ማለት ነው። ጣዖታትንና የጣዖት አምልኮን በተመለከተ ይህን የመሰለ የማንኳሰሻ ስም መስጠት የተለመደ ነው። ኢሳ44፥9-20ን ለምሳሌ ያህል ብቻ መመልከቱ ይበቃል።
50፥3 *ከሰሜን አንድ መንግሥት*፤ በትንቢተ ኤርምያስ ውስጥ ከሰሜን እየተባለ የሚነገርለት ጠላት አብዛኛውን ጊዜ የሚያመለክተው ባቢሎንን ነው (ለምሳሌ 1፥14-15 ይመ)። እዚህ ላይ ግን ቃሉ የሚያመለክተው ምናልባት ፋርስን ሊሆን ይችላል። በባቢሎን ላይ እንዲፈጸም የተወሰነው ቅጣት በእርሷ ላይ ብቻ ተወስኖ የሚቀር ሳይሆን፣ ለተባባሪዎቿ የሰሜን ታላላቅ መንግሥታት ጥምር የሚተርፍ ነው። ይህን ለማመልከት በቍ9 የተጻፉት በ51፥27-28 ላይ በስም ተለይተው ተጠቅሰዋል። *ሰዎችና እንስሳትም ሸሽተው ይሄዳሉ*፤ 33፥12 ይመ።
50፥4 *የእስራኤል ሕዝብና የይሁዳ ሕዝብ*፤ የ3፥18 ማብ ይመ። *እያለቀሱ*፤ ልቅሶውና ዕንባው የንስሐ ልቅሶና ዕንባ ነው (3፥21-22፤ 31፥9 ይመ)።
50፥5 *በዘላለም ቃል ኪዳን*፤ 32፥40 እና ማብ ይመ። እንዲሁም 31፥31-34፤ 33፥20-21 ይመ።
50፥6 *የጠፉ በጎች*፤ በሉቃ15፥3-7 ላይ ጌታ የተናገረውን ምሳሌ ይመ። *እረኞቻቸው*፤ ገዦች (የ2፥8 ማብ ይመ)። *በተራራና በኰረብታ*፤ የአሕዛብ አማልክት የሚመለኩባቸው ቦታዎች (የ2፥20 ማብ ይመ)። *ማደሪያቸውንም*፤ እግዚአብሔርን ራሱን (ቍ7 ይመ)።
50፥7 *የአባቶቻቸውን ተስፋ*፤ 14፥8፡22፤ ዮሐ 28፥20 ይመ።
50፥8 *መንጋ እንደሚመራ የፍየል አውራ*፤ ከባቢሎን ምርኮ በመጀመሪያ ከሚመለሱት መካከል አንዱ ይሁዳ ነው።
50፥9 *የታላላቅ መንግሥታትን ማኅበር*፤ ኢሳ13፥4 ይመ። እዚህ ላይ በጥቅሉ ቢጠቀሱም፣ በ51፥27-28 ላይ ግን በስም ተዘ

*መጥተውም ይይዟታል።*
ቀስቶቻቸው ባዶ እጃቸውን እንደ
ማይመለሱ፣
እንደ ሥልጡን ተዋጊዎች ናቸው።
[10]የባቢሎን ምድር[ገ] ትዘረፋለች፤
የሚዘርፏትም ሁሉ እስኪበቃቸው
ይመዘብሩአታል፤"
ይላል *እግዚአብሔር።*

[11]"እናንተ ርስቴን የበዘበዛችሁ ሆይ፤
ደስ ስላላችሁና ሐሤትም ስላደረጋችሁ፣
በመስክ እንዳለች ጊደር ስለ ፈነጫችሁ፣
እንደ ድንጉላ ፈረስ ስለ አሽካካችሁ፣
[12]እናታችሁ እጅግ ታፍራለች፤
የወለደቻችሁም ትዋረዳለች።
እርሷም ምድረ በዳ፣ ደረቅ ምድርና
በረሓ፣
ከመንግሥታትም ሁሉ ያነሰች
ትሆናለች።
[13]*ከእግዚአብሔር* ቍጣ የተነሣ ባድማ
ትሆናለች እንጂ፣
የሚኖርባት አይገኝም፤
በቍስሎችዋም ሁሉ ምክንያት፣
በባቢሎን የሚያልፍ ሁሉ ይገረማል፤
ያፌዝባታልም።
[14]"እናንተ ቀስት የምትገትሩ ሁሉ፣
በባቢሎን ዙሪያ ተሰለፉ፤
አንዳች ሳታስቀሩ ፍላጻችሁን ስደዱባት፤
*በእግዚአብሔር* ላይ ኀጢአት
ሠርታለችና።
[15]ከየአቅጣጫው ጩኹባት፤
እጇን ትሰጣለች፤ ምሽጓም ይወድቃል፤
ቅጥሮቿ ይፈርሳሉ።
ይህ የ*እግዚአብሔር* በቀል ነውና፣
እርሷን ተበቀሏት፤
በሌሎቹ ላይ እንዳደረገችውም
አድርጉባት።
[16]ከባቢሎን፣ ዘር የሚዘራውን፣
በመከር ጊዜ ማጭድ የጨበጠውንም

50፥10 ኢሳ47፥11፤ ኤር 30፥16
50፥11 ኢሳ47፥6፤ ኤር31፥18
50፥12 ቍ13፤ኢሳ 21፥1፤ኤር25፥12፤ 51፥26:47
50፥13 ቍ3:12፤ ዘዳ29፥22፤ኤር9፥11 ፤18፥16፤48፥9፤ 51፥37:41:62፤ሕዝ 27፥36፤ዕን2፥6
50፥14 ቍ29:42፤ ኢሳ13፥18
50፥15 ቍ28:29፤ 2ነገ25፥4፤መዝ 137፥8፤ኢሳ10፥3፤ 63፥4፤ኤር51፥6:14: 24:44:58፤ዕን2፥7-8፤ ራእ18፥6
50፥16 ኢሳ13፥14፤ ኤር25፥38፤51፥9
50፥17 ዘሌ26፥33፤ ዘኍ24፥8፤ዘዳ4፥27፤ 2ነገ15፥29፤24፥1:17፤ 25፥7፤መዝ119፥176፤ ኤር2፥15፤5፥17፤ 51፥34፤ሰቆ3፥4
50፥18 ኢሳ10፥12 ፤ሕዝ31፥3፤ሶፎ2፥13
50፥19 ኤር31፥5: 10:14፤ሕዝ34፥13፤ ሚክ7፥14፤ዘካ10፥10
50፥20 ዘፍ45፥7፤ መዝ17፥3፤103፥12፤ ኢሳ1፥9፤10፥20-22፤ 33፥24፤38፥17፤ሕዝ 33፥16፤ሚክ7፥18:19 ፤ዘካ3፥4:9፤ሮሜ9፥27
50፥21 ሕዝ23፥23

ዐጭድ አጥፉት፤
ከአጥፊው ሰይፍ የተነሣ፣
እያንዳንዱ ወደ ገዛ ሕዝቡ ይመለስ፤
ወደ ገዛ ምድሩም ይሽሽ።
[17]"እስራኤል አንበሶች ያሳደዱት፣
የተበተነ መንጋ ነው፤
መጀመሪያ የአሦር ንጉሥ፣
በጫጭቆ በላው፤
በኋላም የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር፣
አጥንቱን ቈረጣጠመው።"
[18]ስለዚህ የእስራኤል ስምባክ የሰራዊት ጌታ
*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"የአሦርን ንጉሥ እንደ ቀጣሁት ሁሉ፣
የባቢሎንን ንጉሥና ምድሩን እቀጣለሁ።
[19]እስራኤልንም ወደ መሰማሪያው
እመልሰዋለሁ፤
በቀርሜሎስና በባሳን ላይ ይሰማራል፤
በኤፍሬም ተራሮችና በገለዓድም ላይ፣
እስኪጠግብ ይመገባል።
[20]በነዚያ ጊዜያት፣ በዚያ ዘመን፣"
ይላል *እግዚአብሔር፤*
"የእስራኤል በደል ይፈለጋል፤
አንዳችም አይገኝም፤
የይሁዳም ኀጢአት ይፈለጋል፤
ከቶም የለም፤
እንዲተርፉ ያደረግኋቸውን ትሩፋን
እምራለሁና።
[21]"የምራታይምን ምድር፣
የፋቁድ ነዋሪዎችንም፣
አሳዷቸው፤ ግደሏቸው፤ ፈጽማችሁም
አጥፏቸው፤"[ነ]
ይላል *እግዚአብሔር፤*
"ያዘዝኋችሁንም ሁሉ አድርጉ።

[ገ]10 *ወይም ከለዳውያን*
[ነ]21 *አጥፏቸው* ለሚለው የሚተካው የዕብራይስጡ ቃል የሚያመለክተው ነገሮችን ወይም ሰዎችን ዳግም ላይመለሱ ለእግዚአብሔር ሙሉ በሙሉ መስጠትን ነው፤ ቍ26 ይመ።

ርዝረዋል (ቍ3 ማብ ይመ)። *ባዶ እጃቸውን እንደማይመለሱ፤* ኢሳ55፥11 ይመ።

50፥11 *እናንተ፡* የባቢሎንን ሰዎች ነው። *ርስቴን፡* የእግዚአብሔርን ምድርና ሕዝቡን (2፥7 እንዲሁም 12፥7 እና ማብ ይመ)። *እንዳለች ጊደር ስለ ፈነጫችሁ፡* ሚል4፥2 ይመ። *ድንጉላ ፈረስ፡* የ8፥16 ማብ ይመ።

50፥12 *እናታችሁ፤* አንድም ከተማዪቱን አሊያም ምድሪቱን ያመለክታል (ኢሳ50፥1፤ ሆሴ2፥5 ይመ)። *ያነሰች፤* ቃል በቃል የመጨረሻዋ ማለት ነው። አማሌቅ እስራኤልን ለመውጋት "ከአሕዛብ መካከል የመጀመሪያዋ" (ዘኍ24፥40) ሆናለች፤ እንደዚሁም እስራኤልን ለመውጋት የመጨረሻ የሆነችው ባቢሎን ትጠፋለች።

50፥13 *የሚኖርባት አይገኝም፡* ኢሳ13፥20 እና ማብ ይመ። *በቍስሎቿም ሁሉ ምክንያት … የሚያልፍ ሁሉ ይገረማል፤* ይህ ቃል በ19፥8 ስለ ኢየሩሳሌም፣ በ49፥17 ላይ ደግሞ ስለ ኤዶም ተነግሯል።

50፥14 *ቀስት የምትገትሩ፤* ይህ የሜድን ሰዎች ጭምር ያመለክታል (ኢሳ13፥17-18 ይመ)።

50፥15 *ጩኹባት፤* የጦር ባልደረቦችን ወኔ ለማነሣሣት የሚደረግ (ኢያ6፥16 ይመ)። *የእግዚአብሔር በቀል፤* ቍ28፤ 51፥11 ይመ። ይህ ከቅዱስነቱ አንጻር የሚነገር ቢሆንም፣ በተግባር የሚገለጠው አብዛኛውን ጊዜ በራሱ ሕዝብ አማካይነት ነው (ዘኍ31፥3 ይመ)።

50፥16 *ከአጥፊው ሰይፍ፡* 46፥16 ይመ። *እያንዳንዱ … ወደ ገዛ ምድሩ፤* በዚህ ክፍል የተጻፈው የዕብራይስጥ ቅጅ የኢሳ 13፥14 ጋር ተጓዳኝ ነው። በባቢሎን ምርኮ የተወሰዱት ሕዝቦች ከወራሪዎች ሰይፍ ሸሽተው ማምለጥ እንዳለባቸው የተሰጠ ማስጠንቀቂያ ነው።

50፥17 *የተበተነ መንጋ፡* ኢል3፥2 ይመ። *አንበሶች፤* አንበሳ የአሦርና የባቢሎን ምሳሌ ነው 4፥7፤ ኢሳ15፥9 እና ማብ ይመ። *መጀመሪያ የአሦር ንጉሥ፤* እስራኤልን (የሰሜኑን መንግሥት) በ722-721 ዓ.ቅ.ክ ላይ አሦራውያን አጠፉት። *በኋላም … ናቡከደነፆር፤* ባቢሎናውያን ደግሞ በ586 ዓ.ቅ.ክ ላይ ይሁዳን (የደቡቡን መንግሥት) ደመሰሱት።

50፥18 *የአሦርን ንጉሥ … ቀጣሁት፤* ትዕቢተኛይቱ የአሦር መዲና ነነዌ በ612 ዓ.ቅ.ክ ላይ ወደቀች። አሦር ራሷ ደግሞ ሜዶናውያንና ባቢሎናውያን ግንባር ፈጥረው ስለ ወጓት በ609 ዓ.ቅ.ክ ላይ ድል ሆነች።

50፥19 *በቀርሜሎስና፤* ኢሳ33፥9 እና ማብ ይመ። *በባሳን፤* የኢሳ2፥13 ማብ ይመ። *በኤፍሬም ተራሮችና፤* አረንጓዴ ልምላሜን የተጐናጸፈው የመካከለኛው እስራኤል ተራሮች ወገብ (ሕዝ 34፥13-14 ይመ)። *በገለዓድም፤* ዘኍ32፥1፤ ሚክ7፥14 ይመ።

*50፥20፤* 33፥8 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 36፥3፤ ሚክ 7፥18-19 ይመ።

50፥21 *የምራታይም፡* ትርጕሙ "በእግዚአብሔር ላይ የተደረገ ዕጥፍ ዐመፅ" ማለት ነው። ምናልባት የሚያመለክ ተው ቍ24 እና 29ን ሊሆን ይችላል (መሳ3፥8፤ ኢሳ40፥2 እና ማብ

[22]በምድሪቱ የጦርነት ውካታ፣
የታላቅ ጥፋት ድምፅ ተሰማ::
[23]የምድር ሁሉ መዶሻ፣
እንዴት ተሰበረ! እንዴትስ ደቀቀ!
በሕዝቦች መካከል፣
ባቢሎን እንዴት ባድማ ሆነች!
[24]ባቢሎን ሆይ፤ ወጥመድ ዘርግቼልሻለሁ፤
አንቺም ሳታውቂ ተይዘሻል፤
እግዚአብሔርን ተገዳድረሻልና፣
ተገኘሽ፤ ተያዝሽም::
[25]እግዚአብሔር የመሣሪያ ግምጃ ቤቱን
ከፍቶአል፤
የቍጣውን የጦር ዕቃ አውጥቶአል፤
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፣
በባቢሎናውያን ምድር ሥራ አለውና::
[26]ከሩቅ መጥታችሁ በእርሷ ላይ ውጡ፤
ጐተራዎቿን አፈራርሱ፤
እንደ እህል ክምር ክምሯት፤
ፈጽማችሁ አጥፏት፤
ምንም አይቅር::
[27]ወይፈኖቿን ሁሉ ዕረዱ፤
ወደ መታረጃም ይውረዱ!
የሚቀጡበት ጊዜ፣
ቀናቸው ደርሶአልና ወዮላቸው!
[28]እግዚአብሔር አምላካችን የተበቀለውን፣
ስለ ቤተ መቅደሱ የተበቀለውን በቀል፣
ከባቢሎን የመጡ ኰብላዮችና ስደተኞች፣
በጽዮን የሚናገሩትን ስሟቸው::
[29]"ቀስት የሚገትሩትን፣
ቀስተኞችን ሁሉ በባቢሎን ላይ ጥሩ፤
አንድም ሰው እንዳያመልጥ፣
ዙሪያውን ሁሉ መሽጉ፤
የእስራኤልን ቅዱስ፣
እግዚአብሔርን አቃላለችና፣
እንደ ሥራዋ መጠን መልሱላት፤
በሌሎች ላይ እንዳደረገችውም
አድርጉባት::
[30]ስለዚህ ወንዶች ወጣቶቿ በየአደባባዩ
ይረግፋሉ፤
በዚያ ቀን ወታደሮቿ ሁሉ
ይወድቃሉ፤"
ይላል እግዚአብሔር፤
[31]"አንተ ትዕቢተኛ፤ እነሆ፣ በአንተ ላይ
ተነሥቻለሁ፤"
ይላል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር፤
"የምትቀጣበት ጊዜ፣
ቀንህ ደርሶአልና::
[32]ትዕቢተኛው ይሰናከላል፤ ይወድቃልም፤
የሚያነሣውም የለም፤
በዙሪያው ያሉትን ሁሉ የሚበላ እሳት፣
በከተሞቹ ውስጥ አስነሣለሁ::
[33]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"የእስራኤል ሕዝብና የይሁዳ ሕዝብ፣
በአንድነት ተጨቍነዋል፤
የማረኳቸውም ሁሉ አጥብቀው ይዘዋቸዋል፤
ይለቅቋቸውም ዘንድ እንቢ ብለዋል::
[34]ነገር ግን ቤዛቸው ብርቱ ነው፤
ስሙም የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ነው፤
ለምድራቸው ዕረፍትን ለመስጠት፤
ተግቶ ይሟገትላቸዋል፤
በባቢሎን የሚኖሩትን ግን ዕረፍት
ይነሣቸዋል::
[35]"ሰይፍ በባቢሎናውያን ላይ መጣ!"
ይላል እግዚአብሔር፤
"በባቢሎን ነዋሪዎች ላይ፤
በባለሥልጣኖቿና በጥበበኞቿም ላይ
ተመዘዘ!
[36]ሰይፍ በሐሰተኞች ነቢያቷ ላይ መጣ!
እነርሱም ሞኞች ይሆናሉ፤
ሰይፍ በጦረኞቿ ላይ ተመዘዘ፤
እነርሱም ይሸበራሉ::
[37]ሰይፍ በፈረሰኞቿና በሠረገሎቿ ላይ፣

50፥22 ኤር4፥19-21፤51፥54
50፥23 ኢሳ10፥5፤14፥16፤ኤር51፥25
50፥24 ኢዮ9፥4፤ኤር51፥12:31
50፥25 ኢሳ13፥5፤ኤር51፥25:55
50፥26 ቍ3፥41፤ሩት3፥7፤ኢሳ14፥22-23፤ኤር51፥11
50፥27 ኢዮ18፥20፤መዝ68፥30፤ኢሳ30፥25፤ኤር25፥34፤48፥15፤51፥6
50፥28 ቍ8፥15፤2ነገ24፥13፤ኢሳ48፥20፤ኤር51፥10:11፤52፥13
50፥29 ቍ14፤ዘጸ32፥4፤ኢዮ21፥19፤መዝ78፥41፤ ኢሳ13፥18፤14፥13-14፤41፥20፤47፥10፤ኤር51፥3፡5፡6፤ሕዝ35፥11፤ዳን5፥23፤አብ1፥15፤ራእ18፥6
50፥30 ኢሳ13፥18
50፥31 ኢዮ18፥20፤ኤር21፥13፤ራእ18፥7-8
50፥32 መዝ20፥8፤119፥21፤ኤር49፥27፤አሞ 5፥2
50፥33 ኢሳ14፥17፤58፥6
50፥34 ዘፀ6፥6፤ኢዮ19፥25፤መዝ119፥154፤ኢሳ14፥7፤49፥25፤ኤር15፥21፤31፥35፤51፥19:36፤ሰቆ3፥58
50፥35 ኢሳ45፥1፤ኤር47፥6፤ዳን 5፥7
50፥36 ኤር49፥22፤51፥30:32
50፥37 2ነገ19፥23፤ኢሳ19፥16፤45፥3፤ኤር51፥21

ይመ)::

50፥22 *የታላቅ ጥፋት*፤ 4፥6፤ 6፥1 ይመ:: ከ48፥3፤ ከ51፥54 ጋር ያነጻጽሩ::

*50፥23፤ የምድር ሁሉ መዶሻ፤* የኢሳ10፥5 ማብ ይመ:: *በሕዝቦች መካከል ... እንዴት ባድማ ሆነች!* በዕብራይስጡ ቅጅ ይህ ዐረፍተ ነገር በ51፥41 ላይ ተደግሞአል::

50፥24 *አንቺም ሳታውቂ ተይዘሻል*፤ በ539 ዓ.ቅ.ክ ላይ የፋርስ ጦር ባቢሎንን የሚይዘት ሳታስበው ድንገት መሆኑን የሚ ገልጽ፣ አስቀድሞ የተነገረ ትንቢት (51፥8፤ ኢሳ47፥11 ይመ)::

50፥25 *የቍጣውን የጦር ዕቃ፤* ባቢሎንን ድል ለማድረግ እግዚአብሔር መሣሪያ አድርጎ ይሚጠቀምባቸውን ሕዝቦች (ኢሳ 13፥5 እና ማብ ይመ):: *እግዚአብሔር ... ሥራ አለውና፤* 48፥10 ይመ::

50፥26 *እህል ክምር*፤ በዕብራይስጡ ቅጅ ይህ ሐረግ በነህ 4፥2 ላይ ከቃጠሎ የተረፈውን ስብርባሪ ለመግለጽ ተጠቅሶአል:: *ፈጽማችሁ አጥፏት*፤ በእሳት በማቃጠል የቍ21 ማብ ይመ፤ እን ዲሁም ኢያ11፥11-13 ይመ::

50፥27 *ወይፈኖቿን*፤ የባቢሎን ሕዝብ በተለይ ደግሞ ተዋጊ ሰራዊቱ (ኢሳ34፥6-7 እና ማብ ይመ):: *ወደ መታረጃም ይውረዱ*፤ የ48፥15 ማብ ይመ:: *የሚቀጡበት ጊዜ፤* 11፥23፤ 23፥12፤ 46፥21 ይመ::

50፥28 *ኰብላዮችና ስደተኞች፤* ባቢሎን በጠላት እጅ ወድቃ በጠፋች ጊዜ ሸሽተው ያመለጡ አይሁድ ምርኮኞች:: *ስለ ቤተ መቅደሱ የተበቀለውን በቀል፤* ቍ15 እና ማብ ይመ:: 46፥10፤ 51፥6:: ባቢሎን ለመሸነፍ የበቃችው፣ የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅ ደስ ስላቃጠለች በእግዚአብሔር በቀል ነው::

50፥29 *እንደ ሥራዋ መጠን መልሱላት፤* ከ25፥14 የተስ ተጋባ አባባል (51፥24 ይመ):: *በሌሎች ላይ እንዳደረገችውም አድርጉባት፤* ቍ15 ይመ:: *የእስራኤልን ቅዱስ፤* በትንቢተ ኢሳ ይያስ ተደጋግሞ በእግዚአብሔር የተነገረ ተጨማሪ ስም ነው (የኢሳ 1፥4 ማብ ይመ):: በትንቢተ ኤርምያስ ውስጥ የሚገኘው ግን እዚህና በ51፥5 ላይ ብቻ ነው::

*50፥30፤* በ49፥16 ላይ በአብዛኛው ቃል በቃል ተደግሞአል::

*50፥31-32፤* ከ21፥13-14 የተስተጋባ ሲሆን፣ በ21፥13-14 ላይ የተነገረው ለኢየሩሳሌም ነው፤ በዚህ ስፍራ የተገለጠው ደግሞ ባቢሎንን ያመለክታል::

50፥33 *የማረኳቸውም፤* ኢሳ14፥2 ይመ:: *ይለቋቸውም ዘንድ እምቢ ብለዋል*፤ ፈርዖን በተደጋጋሚ አልለቅም በማለት ያሳየውን የልብ ደንዳናነት ያስታውሳል (ለምሳሌ:- ዘፀ7፥14፤ 8፥2:32፤9፥2:7 ይመ)::

50፥34 *ቤዛቸው፤* 31፥11 እና ማብ ይመ:: ተግቶ ይሟገት ላቸዋል (51፥36 ይመ):: *ዕረፍትን ለመስጠት፤* 31፥2 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ14፥3:7 እና የዘዳ 3፥20፤ ኢሱ1፥13 ማብ ይመ::

*50፥35-38፤* ከሕዝ21 ጋር ያነጻጽሩ::

50፥36 *በሐሰተኞች ነቢያቷ ... ሞኞች ይሆናሉ፤* ኢሳ 44፥25፤ እንዲሁም ዘኍ12፥11 ይመ::

50፥37 *በፈረሰኞቿና በሠረገሎቿ ላይ*፤ ኢሳ43፥17 ይመ፤

በመካከሏ ባሉት ባዕዳን ወታደሮች ሁሉ
ላይ መጣ!
እነርሱም እንደ ሴቶች ይሆናሉ፤
ሰይፍ በሀብት ንብረቷ ላይ መጣ!
ለዝርፊያም ይሆናሉ::
[38]ድርቅ[ን] በውሆቿ ላይ መጣ!
እነሆ፣ ይደርቃሉ፤
ምድሪቱ በፍርሀት በሚሸበሩ አማልክት፣
በጣዖትም ብዛት ተሞልታለችና::

[39]"ስለዚህ የምድረ በዳ አራዊትና የጅብ
መኖሪያ፣
የጉጉትም ማደሪያ ትሆናለች፤
ከእንግዲህ ወዲህ ማንም አይኖርባትም፤
ከትውልድ እስከ ትውልድም
የሚቀመጥባት አይገኝም::
[40]እግዚአብሔር ሰዶምንና ገሞራን፣
በዙሪያቸውም የነበሩትን ከተሞች ያለ
ነዋሪ እንዳስቀራቸው፣"
ይላል እግዚአብሔር::
"እንዲሁ ማንም በዚያ አይኖርም፣
የሚቀመጥባትም አይገኝም::
[41]"እነሆ፣ ሰራዊት ከሰሜን ይመጣል፤
አንድ ኀያል መንግሥትና ብዙ
ነገሥታት፣
ከምድር ዳርቻ ተነሣሥተዋል::
[42]ቀስትና ጦር ይዘዋል፤
ጨካኞች ናቸው፤ ምሕረትም
አያደርጉም፤
በፈረሳቸው እየጋለቡ ሲመጡ፣
ድምፃቸው እንደ ባሕር ሞገድ ይተማል
ያስገመግማል::
አንቺ የባቢሎን ሴት ልጅ ሆይ፤
ለጦርነት እንደ ተዘጋጁ ተዋጊዎች
ይመጡብሻል::
[43]የባቢሎን ንጉሥ ስለ እነርሱ ሰማ፤
እጆቹም በድን ሆኑ፤
ጭንቀት ይዞታል፤
ምጥ እንደ ያዛት ሴት ታሟል::
[44]አንበሳ ከዮርዳኖስ ደኖች ድንገት ወጥቶ፣
ወደ ግጦሽ ሜዳ ብቅ እንደሚል፣
እኔም ባቢሎንን ሳይታሰብ ከምድሯ
አባርራታለሁ፤
የመረጥሁትንም በእርሷ ላይ እሾማለሁ፤
እንደ እኔ ያለ ማን ነው? ማንስ ሊገዳደረኝ
ይችላል?

50፥38 ቍ2፤መዝ 137፥1፤ኢሳ11፥15፤ ኤር51፥13፡36
50፥39 መዝ74፥14 ፤ኢሳ13፥19-22፤ 34፥13-15፤ኤር 51፥37፤ራእ 18፥2
50፥40 ዘፍ19፥24፤ ኤር51፥62፤ማቴ 10፥15
50፥41 ቍ26፤ኢሳ 13፥4፡17፤41፥25፤ ኤር51፥22-28
50፥42 ቍ14፤ኢዮ 30፥21፤ኢሳ5፥30፤ 13፥18፤ 47፥1
50፥43 ኤር6፥22-24፤47፥3
50፥44 ዘኍ16፥5፤ ኢዮ41፥10፤ኢሳ 46፥9፤ኤር12፥5፤ 49፥19
50፥45 መዝ33፥11 ፤ኢሳ48፥14፤ኤር 51፥11
50፥46 መሳ5፥4፤ ኢዮ24፥12፤ኤር49፥ 21፤ ራእ 18፥9-10
51፥1 ኢሳ13፥17፤ ኤር25፥12
51፥2 ኢሳ13፥5፡9፤ 41፥16፤ማቴ3፥12
51፥3 ኤር46፥4፤ 50፥29
51፥4 ኢሳ13፥15፡ 18
51፥5 ዘሌ26፥44፤ ኢሳ54፥6-8፤ሆሴ4፥1
51፥6 ቍ24፡56፤ ዘኍ16፥26፤ዘዳ32፥35 ፤ኢዮ21፥19፤ኢሳ1፥ 24፤48፥20፤ኤር25፥ 14፤50፥15፡27፡29፤ ሰቆ3፥64፤ራእ18፥4
51፥7 ኢሳ51፥22፤ ኤር25፥15-16፤49፥ 12፤ራእ14፥8-10

የትኛውስ እረኛ ሊቋቋመኝ ይችላል?
[45]ስለዚህ እግዚአብሔር በባቢሎን ላይ
ያቀደውን፣
በባቢሎናውያንም ምድር ላይ ያሰበውን
ስሙ፤
ከመንጋው ታናናሹ ተጐትቶ ይወሰዳል፤
በእነርሱም ምክንያት መሰማሪያቸውን
ፈጽሞ ያጠፋል::
[46]በባቢሎን ውድቀት ድምፅ ምድር
ትናወጣለች፤
ጩኸቷም በሕዝቦች መካከል
ያስተጋባል::

# 51

እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፣ በባቢሎንና[ኦ] በምድሯ ላይ፣
የሚያጠፋ ነፋስ አስነሣለሁ::
[2]እንዲያበጥሯትና እንዲያወድሟት፣
ባዕዳንን በባቢሎን ላይ እልካለሁ፤
በመከራዋም ቀን፣
ከበው ያስጨንቋታል::
[3]ቀስተኛው ቀስቱን እስኪገትር፣
የጦር ልብሱንም እስኪለብስ ፋታ
አትስጡት፤
ለወጣቶቿ አትዘኑ፤
ሰራዊቷንም ፈጽማችሁ አጥፉ::[ኮ]
[4]በባቢሎን[ኸ] ምድር ታርደው፣
በአደባባዮቿም እስከ ሞት ቈስለው
ይወድቃሉ::
[5]ምድራቸው[ወ] በእስራኤል ቅዱስ ፊት፣
በበደል የተሞላች ብትሆንም፣
እስራኤልንና ይሁዳን ስሞቻቸው፣
የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
አልጣላቸውም::

[6]"ከባቢሎን ሸሽታችሁ ውጡ!
ፈጥናችሁም ሕይወታችሁን አትርፉ!
በኀጢአቷ ምክንያት አትጥፉ::
የእግዚአብሔር በቀል ጊዜ ነው፤
እርሱም የሥራዋን ይከፍላታል::
[7]ባቢሎን በእግዚአብሔር እጅ የወርቅ ጽዋ
ነበረች፤

[ን]38 ወይም ሰይፍ
[ኦ]1 ሌብ ካማይ የከላውዴዎን ማለትም የባቢሎን ስም ነው::
[ኮ]3 አጥፉ ለሚለው የዕብራይስጡ ቃል የሚያመለክተው ነገሮችን ወይም ሰዎችን ዳግም ሳይመለሱ ለእግዚአብሔር ሙሉ በሙሉ መስጠት ነው::
[ኸ]4 ወይም ከላውዴዎን
[ወ]5 ወይም የባቢሉናውያን ምድር

እንዲሁም መዝ20፥7 ይመ:: *ባዕዳን፤* 25፥20፡24፤ ነህ13፥3 ይመ:: *ሴቶች ይሆናሉ፤* ናሆ3፥13 ይመ::

50፥38 *በጣዖትም ብዛት፤* 51፥52 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ 21፥9 ማብ ይመ:: *በፍርሀት በሚሸበሩ፤* 25፥16 እና ማብ ይመ::

*50፥39፤* 2ሳሙ13፥20-22 እና ማብ ይመ::

*50፥40፤* በ49፥18 ላይ የተጠቀሰው በአብዛኛው ተደግሞአል፤ የዚያኑ ማብ ይመ::

*50፥41-43፤* በ6፥22-24 ላይ የተጠቀሰው (ማብ ይመ) በአብዛኛው ተደግሞአል:: ቀደም ሲል ኢየሩሳሌምን በተመለከተ የመጣው ቃል እዚህ ላይ ለባቢሎን ተነግሮ ይታያል::

*50፥44-46፤* ይህ ክፍል ከሞላ ጐደል ቃል በቃል በ49፥19-21 (ማብ ይመ) ተደግሞ ይታያል:: ለኤዶም ተነግሮ የነበረው ንግር በዚህ ስፍራ ለባቢሎን ተነግሮ ይገኛል::

51፥1 *የሚያጠፋ ነፋስ፤* 1ዜና5፥26፤ ሐጌ1፥14 ይመ:: *የሚያጠፋ፤* የ4፥7 ማብ ይመ:: እዚህ ላይ "የሜዶንን መንግሥታት" ይጨምራል (ቍ11)::

51፥3 *ፈጽማችሁ አጥፉ፤* 25፥9፤ 50፥21፡26 ይመ::

51፥4 *በአደባባዮቿም ... ይወድቃሉ፤* 49፥26፤ 50፥30 ይመ::

51፥5 *አልጠላቸውም፤* ቃል በቃል ሲተረጐም ባሏ እንደ ሞተባት፣ ትዳሯ እንደ ተፈታባት ሴት ፈጽሞ አልተዋትም ማለት ነው ከኢሳ54፥4፡6-7 እና ማብ ጋር ያነጻጽሩ:: *በእስራኤል ቅዱስ ፊት፤* የ50፥29 ማብ ይመ::

51፥6 *ሸሽታችሁ ውጡ! ... ፈጥናችሁም ሕይወታችሁን አትርፉ፤* ቍ45፤ 48፥6 ይመ፤ ይህ በ50፥8 ላይ ስለ ይሁዳ ሕዝብ ተነግሮአል:: *የእግዚአብሔር በቀል ...፤* የ50፥15 ማብ ይመ:: *የሥራዋን፤* ኢሳ59፥18፤66፥6 ይመ::

*51፥7፤* 25፥15-16 እና ማብ ይመ:: *ባቢሎን የወርቅ ...፤*

ምድርንም ሁሉ አሰከረች::
ሕዝቦች ከወይን ጠጇ ጠጡ፤
ስለዚህ አሁን አብደዋል::
[8]ባቢሎን በድንገት ወድቃ ትሰበራለች፤
ዋይ በሉላት!
ምናልባት ልትፈወስ ስለምትችል፣
ለቍስሏ የሚቀባ መድኀኒት ፈልጉላት::
[9]“ ‘ባቢሎንን ለመፈወስ ሞክረን ነበር፤
እርሷ ግን ልትፈወስ አትችልም፤
ፍርዷ እስከ ሰማይ ስለ ደረሰ፣
እስከ ደመናም ድረስ ከፍ ስላለ፣
ትተናት ወደየአገራችን እንሂድ::’
[10]“ ‘እግዚአብሔር ቅንነታችንን መሰከረ፤
ኑ፤ ስምሳከኛን እግዚአብሔር ያደረገውን፣
በጽዮን እንናገር::’
[11]“ፍላጻችን ሳሉ፤
ጋሻዎችን አዘጋጁ፤
የእግዚአብሔር ሐሳብ ባቢሎንን ለማጥፋት
ስለ ሆነ፣
የሜዶንን ነገሥታት አነሣሥቶአል፤
እግዚአብሔር ይበቀላል፤
ስለ ቤተ መቅደሱ ይበቀላል::
[12]በባቢሎን ቅጥር ላይ ዐላማ አንሡ!
ጥበቃውን አጠናክሩ፤
ዘብ ጠባቂዎችን አቁሙ፤
ደፈጣ ተዋጊዎችን አዘጋጁ!
እግዚአብሔር በባቢሎን ሕዝብ ላይ
የወሰነውን፣
ዐላማውን ያከናውናል::
[13]አንቺ በብዙ ውሃ አጠገብ የምትኖሪ፣
በሀብትም የበለጸግሽ ሆይ፤
የምትወገጂበት ጊዜ ወጥቶአል፤
ፍጻሜሽ ደርሶአል::
[14]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ
ሲል በራሱ ምሎአል፤
ብዛቱ እንደ አንበጣ መንጋ የሆነ
ሰራዊት ያጥለቀልቅሻል፤
እነርሱም በድል አድራጊነት በላይሽ
ያቅራራሉ::
[15]“ምድርን በኀይሉ የሠራ፣
ዓለምን በጥበቡ የመሠረተ፣
ሰማያትንም በማስተዋሉ የዘረጋ እርሱ
ነው::
[16]ድምፁን ባንጐደጐደ ጊዜ በሰማይ ውሆች
ይናወጣሉ፤
ጉሙን ከምድር ዳርቻ ወደ ላይ
እንዲወጣ ያደርገዋል፤
መብረቅን ከዝናብ ጋር ይልካል፤
ነፋስንም ከግምጃ ቤቱ ያወጣል::
[17]“እያንዳንዱ ሰው ጅልና ዕውቀት
የለሽ ነው፤
የወርቅ አንጥረኛው ሁሉ በሠራው
በጣዖቱ ዐፍሮአል፤
የቀረጻቸው ምስሎቹ የሐሰት ናቸው፤
እስትንፋስ የላቸውም::
[18]እነርሱ ከንቱ የፌዝ ዕቃዎች ናቸው፣
ፍርድ ሲመጣባቸው ይጠፋሉ::
[19]የያዕቆብ ዕድል ፈንታ የሆነው ግን እንደ
እነዚህ አይደለም፤
እርሱ የሁሉ ነገር ፈጣሪ ነውና፤
እስራኤልም የርስቱ ነገድ ነው::
ስሙ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር
ነው::
[20]“አንቺ የእኔ ቈመጥ፣
የጦር መሣሪያዬ ነሽ፤
በአንቺ ሕዝቦችን እሰባብራለሁ፤
በአንቺ መንግሥታትን አጠፋለሁ፤
[21]በአንቺ ፈረሱንና ፈረሰኛውን
እሰባብራለሁ፤
በአንቺ ሠረገላውንና ሠረገላ ነጂውን
እሰባብራለሁ፤
[22]በአንቺ ወንዱንና ሴቱን እሰባብራለሁ፤
በአንቺ ሽማግሌውንና ወጣቱን
እሰባብራለሁ::
በአንቺ ጕረምሳውንና ኰረዳዪቱን
እሰባብራለሁ::
[23]በአንቺ እረኛውንና መንጋውን
እሰባብራለሁ፣
በአንቺ ገበሬውንና በሬውን
እሰባብራለሁ፤
በአንቺ ገዦችንና ባለ ሥልጣኖችን

51፥8 ኢሳ14፥15፤ 21፥9፤ኤር8፥22፤ 46፥11፤ራእ14፥8
51፥9 ኢሳ13፥14፤ 31፥9፤ኤር50፥16፤ ራእ 18፥4-5
51፥10 መዝ64፥9፤ ኤር50፥28፤ሚክ7፥9
51፥11 ቍ-28፤ዘሌ 26፥25፤ኢሳ13፥3፤ 21፥5፤41፥2:25፤ኤር 50፥9:28:45
51፥12 ቍ-27፤ 2ሳሙ-18፥24፤መዝ 20፥5፤ 33፥11፤ኤር 50፥24፤ሕዝ33፥2
51፥13 ኢሳ45፥3፤ ኤር50፥3:38፤ሕዝ 22፥27፤ዕን2፥9
51፥14 ቍ-27፤ዘፍ 22፥16፤ኤር50፥15፤ አሞ6፥8፤7፥1፤ ናሆ 3፥15
51፥15 ዘፍ1፥1፤ መዝ104፥2:24፤ 136፥15
51፥16 ዘዳ28፥12፤ ኢዮ28፥26፤መዝ 135፥7፤18፥11-13፤ ዮና1፥4
51፥17 ኢሳ44፥20 ፤ ዕን2፥18-19
51፥18 ኤር18፥15
51፥19 ዘፀ34፥9፤ መዝ119፥57
51፥20 ኢዮ 34፥24፤ኢሳ10፥5፤ 45፥1፤ ሚክ 4፥13፤ ዘካ 9፥13
51፥21 ዘፀ 15፥1፤ ኢሳ 43፥17፤ ኤር 50፥37
51፥22 2ዜና 36፥17፤ ኢሳ 13፥17-18
51፥23 ቍ-57

የዳን2፥32-43 ማብ ይመ::

51፥8 *ባቢሎን ... ወድቃ፤* ኢሳ21፥9 እና ማብ ይመ:: *የሚቀባ መድኃኒት፤* የ8፥22 ማብ ይመ::

51፥9 ተናጋሪዎቹ በባቢሎን የተወረሩ መንግሥታት ናቸው:: *ወደየአገራችን እንሂድ፤* 50፥16 እና ማብ ይመ:: *ፍርዷ፤* የምትቀጣበት ኀጢአት:: *እስከ ሰማይ ስለ ደረሰ፣ እስከ ደመናም ድረስ ከፍ ስላለ፤* እዚህ ላይ ነቢዩ በቅኔያዊ አገላለጽ ተጠቅሞአል (ዘዳ1፥28፤ መዝ57፥10፤ 108፥4 ይመ)::

*51፥10፤* ተናጋሪው ይሁዳ ነው (50፥28 ይመ):: እግዚአብሔር ቅንነታችንን መሰከረ፤ መዝ37፥8 ይመ::

51፥11 *አነሣሥቶአል፤* ቃል በቃል ሲተረጐም “የሚያጠፋ ነፋስ አስነሣለሁ” ማለት ነው (የቍ-1 ማብ ይመ):: *የሜዶንን፤* ቍ-28፤ ኢሳ13፥17 እና ማብ ይመ:: ኢሳ21፥2፤ ዳን5፥28:31፤ 6፥8:12:15፤ 8፥20 ይመ:: *ይበቀላል፤ ስለ ቤተ መቅደሱ ይበቀላል፤* የ50፥28 ማብ ይመ::

51፥12 *ደፈጣ ተዋጊዎችን አዘጋጁ፤* ተዋጊው ሰራዊት አፈግፍጎ ወደ ምሽጉ እንዳይገባ ነው (ኢያ8፥14-22፤ መሳ20፥29-39 ይመ)::

51፥13 *በብዙ ውሃ፤* የባቢሎን ወንዞች (መዝ 137፥1)፣ እንዲሁም ታላቁ የኤፍራጥስ ወንዝ አስደናቂና ግዙፍ ከሆኑት የመስኖ ቦዮች ጋር በአንድነት መነገራቸው ምሳሌያዊ ነው:: *የምትወገጂበት፤* ከሸማኔ መጠቅለያ ተቈርጦ እንደሚጣል ክር ነው (ኢሳ38፥12 ይመ)::

51፥14 *በራሱ ምሎአል፤* የዘፍ22፥16 ማብ ይመ:: *እንደ አንበጣ ...፤* 46፥23 ይመ:: *በድል አድራጊነት ... ያቅራራሉ፤* የ48፥33 ማብ ይመ::

*51፥15-19፤* ይህ ክፍል ከ10፥12-16 ላይ በአብዛኛው ቃል በቃል የተደገመ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)::

*51፥20-23፤* በድግግሞሽ ውጤታማነት ላይ ኤርምያስ የነበረውን እምነት ያሳያል (4፥23-26 ይመ፤ እንዲሁም በመግቢያው ርእስ ሥር የሥነ ጽሑፉ ገጽታ የሚለውን ይመ)::

51፥20 የእኔ ቈመጥ፤ ከምሳ25፥18 ጋር ያነጻጽሩ፤ ነገሩ በአንድ በኩል ሲታይ፣ (1)የፋርሱ ቂሮስ በቶሎ ባቢሎንን ድል እንደሚያደርግ የሚያሳይ ሊሆን ይችላል፤ (2)ወይም የነገሥታትን አጥፊ (50፥23 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ10፥5 ማብ ይመ) ሊያመለክት ይችላል:: ሁለተኛው አማራጭ የተሻለ አማራጭ እንደ ሆነ

እሰባብራለሁ::

[24]“በጽዮን ላይ ስላደረሱት ጥፋት ሁሉ ለባቢሎንና በባቢሎን[o] ለሚኖሩት ሁሉ ዐይናችሁ እያየ ዋጋቸውን እከፍላቸዋለሁ” ይላል *እግዚአብሔር*::

[25]“አንቺ ምድርን ሁሉ ያጠፋሽ፣
አጥፊ ተራራ ሆይ፤ እኔ በአንቺ ላይ ነኝ፣”
ይላል *እግዚአብሔር*፤
“እጄን በአንቺ ላይ እነሣለሁ፤
ከገመገም ቍልቍል አንከባልልሻለሁ፤
የተቃጠለም ተራራ አደርግሻለሁ::
[26]ከአንቺ ለማእዘን የሚሆን ድንጋይ፣
ለመሠረትም የሚሆን ዐለት
አይወሰድም፤
ለዘላለም ባድማ ትሆኛለሽ፤”
ይላል *እግዚአብሔር*::
[27]“በምድር ሁሉ ላይ ሰንደቅ ዐላማ አንሡ!
በሕዝቦች መካከል መለከት ንፉ!
ሕዝቦችን ለጦርነት በእርሷ ላይ አዘጋጁ፤
የአራራትን፣ የሚኒንና የአስከናዝን
*መንግሥታት*፣
ጠርታችሁ በእርሷ ሰብስቧቸው፤
የጦር አዝማች ሹሙባት፤
ፈረሶችንም እንደ አንበጣ መንጋ
ስደዱባት::
[28]የሜዶንን ነገሥታት፣
ገዦቿንና ባለሥልጣኖቿን ሁሉ፣
በግዛታቸው ሥር ያሉትን አገሮች ሁሉ፣
እነዚህን ሕዝቦች ለጦርነት
አዘጋጁባት::
[29]ሰው በዚያ መኖር እስከማይችል ድረስ፣
የባቢሎንን ምድር ባድማ ለማድረግ፣
*እግዚአብሔር* በባቢሎን ላይ ያቀደው
ስለሚጸና፣
ምድር ትናወጣለች፤ በሥቃይም
ትወራጫለች::

51፥24 ቍ6:35፤ ዘጸ 32፥41፤ ኤር 50፥15፤ ሰቆ 3፥64፤ ኢሳ 45፥1
51፥25 ዘፀ 3፥20፤ ኤር 21፥13፤ 50፥23፤ ዘካ 4፥7
51፥26 ቍ29፤ ኢሳ 13፥19-22፤ ኤር 50፥12
51፥27 ቍ14፤ ዘፍ 8፥43፤ 10፥3፤ መዝ 20፥5፤ ኢሳ 13፥2፤ ኤር 25፥14
51፥28 ቍ 11:48
51፥29 ቍ43፤ መሳ 5፥4፤ መዝ 33፥11፤ ኢሳ 13፥20፤ ኤር 48፥9፤ 49፥21
51፥30 ኢሳ 19፥16፤ 45፥2፤ 47፥14፤ ኤር 50፥36
51፥31 2ሳሙ 18፥19-31፤ኤር 50፥2፤ዳን5፥30
51፥32 ኢሳ47፥14፤ ኤር50፥36
51፥33 ኢሳ13፥22፤ 17፥5፤21፥10፤47፥1
51፥34 ቍ44፤ ዘሌ 18፥25፤ኤር50፥17፤ ሆሴ8፥8፤ናሆ2፥12
51፥35 ቍ24፤መዝ 137፥8፤ኢል3፥19፤ ዕን 2፥17
51፥36 ቍ6፤መዝ

[30]የባቢሎን ጦረኞች መዋጋት ትተዋል፤
በምሽጎቻቸው ውስጥ ተቀምጠዋል፤
ኀይላቸው ተሟጦአል፤
እንደ ሴት ሆነዋል፤
በማደሪያዎቿም እሳት ተለኵሶአል፤
የደጃም መወርወሪያ ተሰብሮአል::
[31]ከተማዪቱ ሙሉ በሙሉ መያዟን፣
ለባቢሎን ንጉሥ ለመንገር፣
አንዱ ወሬኛ ሌላውን ወሬኛ፣
አንዱ መልእክተኛ ሌላውን መልእክተኛ
ወዲያው ወዲያው ይከተላል፤
[32]*መልካዎቿ እንደተያዙ*፣
የወንዝ ዳር ምሽጎቿ እንደ ተቃጠሉ፣
ወታደሮቿም እንደ ተደናገጡ ሊነግሩት
ይሯሯጣሉ::”

[33]የእስራኤል አምላክ የሰራዊት ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

“የባቢሎን ሴት ልጅ በመረገጥ ላይ
እንዳለ፣
የእህል መውቂያ አውድማ ናት፤
የመከር ወራቷም ፈጥኖ ይደርስባታል::

[34]“የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በላን፣
አድቅቆ ፈጨን፤
እንደ ባዶ ማድጋ አደረገን፤
እንደ ዘንዶ ዋጠን፣
እንደ ጣፋጭ በልቶን ሆዱን ሞላ፤
በኋላም አንቅሮ ተፋን፤
[35]የጽዮን ነዋሪዎች፣ እንዲህ ይላሉ፤
“በሥጋችን[u] ላይ የተፈጸመው ግፍ
በባቢሎን ላይ ይሁን፤”
ኢየሩሳሌም እንዲህ ትላለች፤
“ደማችን በባቢሎን ምድር በሚኖሩት
ላይ ይሁን::”

[36]ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

[o]24 ወይም *ከላውዴዎን፤* ቍ35 ይመ::
[u]35 ወይም *በእኛና በልጆቻችን ላይ የተፈጸመው*

ይታሰባል:: *እሰባብራለሁ፤* ቍ21-23 ይመ::

51፥24 *ዐይናችሁ እያየ፤* የይሁዳን ሕዝብ ነው:: *ስላደረሱት ጥፋት ሁሉ ... እከፍላቸዋለሁ፤* ቍ6፤ 50፥15:29 ይመ::

51፥25 *አጥፊ ተራራ፤* ኀያላን መንግሥታትን በምሳሌ የሚገልጥ ሐረግ ነው (ዳን2፥35:44-45 ይመ)፤ እዚህ ላይ የሚያመለክተው ባቢሎን ነው:: *የተቃጠለም ተራራ፤* ባቢሎን እግዚአብሔር ከፈረደባት በኋላ፣ ፈንድቶና ነዶ እንዳበቃለት እሳተ ገሞራ ትሆናለች::

51፥26 *ለዘላለም ባድማ፤* 25፥12፤ 50፥12-13 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ13:20 ማብ ይመ::

*51፥27፤* 50፥29 ይመ:: *ሰንደቅ ዐላማ አንሡ! ... መለከት ንፉ፤* 4፥5-6፤ 6፥1 እና ማብ ይመ:: *ለጦርነት ... አዘጋጁ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም “ተገቢና ተስማሚ የሆኑትን ሰዎች ለዩ” ማለት ነው (የ6፥4 ማብ ይመ):: *መንግሥታት፤* ከሜዶን መንግሥት ጋር ያበሩ (ቍ11 እና ማብ ይመ):: *አራራት፤* የዘፍ8፥4 ማብ ይመ:: *ሚኒ፤* በአሦር የቅርጻ ቅርጽ ጽሑፍ ላይ እንደ ተገለጸው፣ የአንድ ክፍለ አገር ስም ሲሆን፣ የሚገኘውም በአርማንያ ውስጥ ነው:: *አስከናዝ፤* የዘፍ10፥3 ማብ ይመ:: *አዝማች፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ ቅጅ ከዚህ ሌላ የሚገኘው ናሆ3፥17 ላይ ብቻ ነው፤ ትርጕሙም (“ሹማምንት”) የሚል ነው:: ቃሉ ከባቢሎናውያን ቋንቋ የተወረሰ ሲሆን፣ ቃል በቃል ሲተረጐምም ጸሓፊ ማለት ነው:: *እንደ አንበጣ ...፤* የ46፥23 ማብ ይመ::

51፥28 *ሜዶን፤* የቍ11 ማብ ይመ:: *በግዛታቸው ሥር ያሉትን አገሮች ሁሉ፤* የ34፥1 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 1ነገ9፥19 ይመ::

51፥29 *ምድር ትናወጣለች፤ በሥቃይም ትወራጫለች፤* ገና ለገና ጦርነት ይመጣል በማለት::

51፥30 *ኀይላቸው ተሟጦአል፤ ... ሴት፤* በዕብራይስጥ ቋንቋ በቃላት ጨዋታ ምሥጢር መናገር የተለመደ ነው:: *እንደ ሴት ሆነዋል፤* 50፥37፤ ናሆ3፥13 ይመ::

51፥31 *አንዱ ወሬኛ ሌላውን ... ይከተላል፤* ከየከተማው ሁሉ ወደ ቤተ መንግሥቱ ወሬ ይዘው ይሽቀዳደማሉ::

51፥32 *መልካዎቿ፤* ወንዞችን በእግር ወይም በመኪና ለማቋረጥ የማያስችሉ ጠባብ ስፍራዎች፣ ወይም በእግር መሻገር በማይቻልባቸው አቅጣጫዎችም ጀልባዎች ዝግጁ ሆነው የሚጠባበቁባቸው በታዎች ናቸው:: *ምሽጎቿ እንደ ተቃጠሉ፤* ሸንበቆዎችን ጨርሶ ለማጥፋትና ከአደጋው ለማምለጥ የሚሸሹ ሰዎች መደበቂያ እንዳያገኙ ለማድረግ::

51፥33 *የባቢሎን ሴት ልጅ፤* 50፥42 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ47፥1 ማብ ይመ:: *አውድማ፤* የአንዲት ከተማ ወይም የአንድ ሕዝብ መጥፋት አብዛኛውን ጊዜ እህል ታጭዶና ተወቅቶ በጐተራ በሚገባበት ወቅት እየተመሰለ ትንቢት ተነግሮአልል (ኢሳ27፥12፤ ኢዮ3፥13፤ ሚክ4፥12-13 ይመ)::

51፥34 *ዘንዶ፤* የኢሳ 51፥9 ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ 1፥21 ማብ ይመ::

51፥35 *በሥጋችን፤* ሚክ3፥2-3 ይመ::

"እነሆ፤ እሟገትልሻለሁ፣
በቀልሽንም እኔ እበቀልልሻለሁ፤
ባሕሯን አደርቃለሁ፣
የምንጮቿንም ውሃ።
[37]ባቢሎን የፍርስራሽ ክምር፣
የቀበሮዎች መፈንጫ፣
የድንጋጤና የመሣለቂያ ምልክት
ትሆናለች፤
የሚኖርባትም አይገኝም።
[38]ሕዝቦቿ ሁሉ እንደ ደቦል አንበሳ
ያገሣሉ፤
እንደ አንበሳ ግልገልም ያጒረመርማሉ።
ጒሮሮአቸው በደረቀ ጊዜ
ድግስ አዘጋጅላቸዋለሁ፤
እንዲሰክሩም አደርጋቸውና፣"
[39]በሣቅ እየፈነደቁ፣
ለዘላለም ሳይነቁ ይተኛሉ።"
ይላል *እግዚአብሔር*።
[40]"እንደ ጠቦት፣
እንደ አውራ በግና እንደ ፍየል፣
ወደ መታረድ አወርዳቸዋለሁ።
[41]"ሼሻክ* እንዴት ተማረከች!
የምድር ሁሉ ትምክህትስ እንዴት
ተያዘች!
ባቢሎን በሕዝብ ሁሉ ዘንድ፣
ምንኛ አስደንጋጭ ሆነች።
[42]ባሕር በባቢሎን ላይ ይወጣል፤
ሞገዱም እየተመመ ይሸፍናታል።
[43]ከተሞቿ ሰው የማይኖርባቸው፣
ዘርም የማይልባቸው፣
ደረቅና በረሓማ ቦታ፣
ባድማ ምድርም ይሆናሉ።
[44]ቤልን በባቢሎን ውስጥ እቀጣለሁ፤
የዋጠውን አስተፋዋለሁ፤
ሕዝቦች ከእንግዲህ ወደ እርሱ
አይጐርፉም፤
የባቢሎንም ቅጥር ይወድቃል።
[45]"ሕዝቤ ሆይ፤ ከመካከሏ ውጡ!
ሕይወታችሁን አትርፉ!
ከአስፈሪው የ*እግዚአብሔር* ቍጣ
አምልጡ።
[46]ወሬ በምድሪቱ ሲሰማ፣
ተስፋ አትቍረጡ ፤ አትፍሩም፤
ገዥ በገዥ ላይ ስለ መነሣቱ፣
ዐመፅም በምድሪቱ ስለ መኖሩ፣
አንድ ወሬ ዘንድሮ፣ ሌላውም ለከርሞ
ይመጣል፤
[47]የባቢሎንን ጣዖታት የምቀጣበት ጊዜ፣
በእርግጥ ይመጣልና።
ምድሯ በሙሉ ትዋረዳለች፤
የታረዱትም በሙሉ በውስጧ
ይወድቃሉ።
[48]ሰማይና ምድር በውስጣቸውም ያለው
ሁሉ፣
በባቢሎን ላይ እልል ይላሉ፤
አጥፊዎች ከሰሜን ወጥተው፣
እርሷን ይወጓታልና፣"
ይላል *እግዚአብሔር*።
[49]"በምድር ሁሉ የታረዱት፣
በባቢሎን ምክንያት እንደ ወደቁ፣
ባቢሎንም በእስራኤል በታረዱት
ምክንያት መውደቅ ይገባታል።
[50]ከሰይፍ ያመለጣችሁ ሆይ፤
ሂዱ! ጊዜ አትፍጁ፤
በሩቅ ምድር ያላችሁ *እግዚአብሔርን*
አስታውሱ፤
ኢየሩሳሌምንም አስቧት።"
[51]"ባዕዳን ሰዎች ወደ ተቀደሰው፣
ወደ *እግዚአብሔር* ቤት ስለ ገቡ፣
እኛ ተሰድበናል፤
ዕፍረትም ፊታችንን ሸፍኖአል፤
ውርደትም ተከናንበናል።"
[52]"እንግዲህ ጣዖቶቿን የምቀጣበት ዘመን
ይመጣል፣"
ይላል *እግዚአብሔር*፤
"በምድሯም ሁሉ፤

*41 *ሼሻክ* የባቢሎን ስውር ስም ነው።

140፥12፤ኢሳ11፥15፤ 19፥5፤ኤር20፥12፤ 50፥34፤ሰቆ3፥58፤ ሆሴ13፥15፤ሮሜ 12፥19
51፥37 ኢሳ13፥22፤ ኤር50፥13፡39፤ናሆ 3፥6፤ሚል2፥9፤ራእ 18፥2፤
51፥38 ኢሳ5፥29
51፥39 ቍ57፤መዝ 13፥3፤ኢሳ 21፥5፤ ኤር50፥24
51፥40 ሕዝ39፥18
51፥41 ኢሳ13፥19፤ ኤር 25፥26፤ 50፥13
51፥42 መዝ18፥4፤ ኢሳ 8፥7
51፥43 ቍ29:62፤ ኢሳ 13፥20፤ 21፥1፤ ኤር 2፥6
51፥44 ቍ34:58፤ 2ነገ25፥4፤ኢሳ21፥9፤ 25፥12፤46፥1፤ኤር 50፥15
51፥45 ቍ50፤ መዝ76፥10፤ 79፥6፤ ኢሳ 48፥20
51፥46 2ነገ19፥7፤ መዝ18፥45፤ኤር 46፥27
51፥47 ኢሳ46፥1-2 ፤ኤር27፥7፤50፥2:12
51፥48 ቍ11:53: 56፤ኢዮ 3፥7፤መዝ 149፥2፤ኢሳ41፥25፤ ኤር25፥26፤ ራእ 18፥20
51፥49 መዝ137፥8 ፤ ኤር 50፥29
51፥50 ቍ45፤ መዝ137፥6፤ኤር 23፥23
51፥51 መዝ44፥13- 16፤79፥4፤ሰቆ 1፥10
51፥52 ቍ47፤ኢዮ 24፥12

51፥36 *እበቀልልሻለሁ፤* ቍ6:11 ይመ፤ እንዲሁም የ50፥15 ማብ ይመ። *ባሕሯን ... የምንጮቿንም፤* የቍ13 ማብ ይመ። በኢሳ21፥1 ላይ ባቢሎን፣ "በባሕር አጠገብ ያለች ምድረ በዳ" ተብላ ተጠርታለች (የዚያኑ ማብ ይመ)።

*51፥37፤* 9፥11፤ 18፥16 እና ማብ ይመ።

51፥38 *እንደ ደቦል አንበሳ ያገሣሉ፤* 2፥15 እና ማብ ይመ።

51፥40 *ጠቦት ... አውራ በግና ... ፍየል፤* ስለ ባቢሎን ሕዝብ በምሳሌነት የተነገሩ ቃላት (ኢሳ34፥6፤ ዕዝ39፥18 ይመ)። *መታረድ፤* ዘዳ32፥24፤ ኢሳ13፥22 ይመ።

51፥41 *ሼሻክ፤* የ25፥26 ማብ ይመ።

51፥42 *ባሕር ... ሞገዱም፤* ኢሳ17፥12 እና ማብ ይመ። እዚህና በቍ55 ላይ የተጻፈው የባቢሎንን ጠላቶች የሚያመለክት ነው (46፥7 እና ማብ ይመ)።

*51፥43፤* 48፥9፤ 49፥18:33፤ 50፥12-13 ይመ።

51፥44 *ቤልን፤* 50፥2፤ ኢሳ46፥1 እና ማብ ይመ። *የዋጠውን፤* ይሁዳን ጨምሮ በምርኮ የወሰዳቸውን ሕዝቦች፣ ከኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ ያዕዛቸውን ንዋያተ ቅድሳትና ባጠቃላይ ከአገሪቱ አግበስብሶ የወሰደውን የምርኮ ዕቃ (ዳን5፥2-3 ይመ)። *የባቢሎን ቅጥር፤* ሁለት ዙር የግንብ አጥር፣ በስተ ውጭ በኩል ያለው ውፍረቱ ስድስት ክንድ ያህል ሲሆን፣ በስተ ውስጥ በኩል ያለው ደግሞ ውፍረቱ ዐሥር ክንድ ተኩል ያህል ነው። በሁለቱ ቅጥሮች መካከልም አስፈላጊ ሲሆን በውሃ የሚሞላ ዐሥራ አንድ ክንድ ያህል ስፋት ያለው ደረቅ ቦይ አለ።

51፥45 *ሕይወታችሁን አትርፉ፤* የቍ6 ማብ ይመ። *ከአስፈሪው ... ቍጣ፤* 4፥8:26፤ ኢሳ13፥13፤ ናሆ1፥6 ይመ።

51፥46 *ወሬ ... ሲሰማ ... አትፍሩም፤* ጌታ በደብረ ዘይት ተራራ ላይ ረጅም ንግግር ባደረገ ጊዜ (ማቴ24፥6፤ ማር 13፥7፤ ሉቃ 21፥9 ይመ) ይህን ቃል ሳያስታውስ አልቀረም።

51፥47 *የባቢሎንን ጣዖታት የምቀጣበት፤* ቍ52 ይመ፤ እንዲሁም የ50፥2 ማብ ይመ።

51፥48 *ሰማይና ምድር ... እልል ይላሉ፤* ኢሳ44፥23፤ ራዕ18፥20፤ 19፥1-3 ይመ። *ከሰሜን ወጥተው፤* የ50፥3 ማብ ይመ።

*51፥49፤* የ25፥26 ማብ ይመ።

51፥50 *ሂዱ፤* የቍ6 ማብ ይመ።

51፥51 *ባዕዳን ሰዎች ወደ ተቀደሰው ወደ እግዚአብሔር ቤት ስለ ገቡ፤* ናቡከደነፆር 586 ዓ.ቅ.ክ ላይ በኢየሩሳሌም የነበረውን ቤተ መቅደስ ማርከሱን የሚያመለክት ነው። አንጥያኮስ ኢጲፋኒዮስ በ168 ዓ.ቅ.ክ ላይ፣ ሮማውያንም በ70ዓ.ም ቤተ መቅደሱን እንደዚሁ አርክሰውታል።

51፥52 *ጣዖቶቿን የምቀጣበት፤* የ50፥2 ማብ ይመ።

ቍስለኞች ያቃስታሉ።

[53]ባቢሎን ወደ ሰማይ ብትወጣም፣
ከፍ ያለ ምሽጓን ብታጠናክርም፣
አጥፊዎች እሰድባታለሁ፤"
ይላል እግዚአብሔር።

[54]"ከባቢሎን ጩኸት፣
ከባቢሎናውያንም[1] ምድር፣
የታላቅ ጥፋት ድምፅ ይሰማል።
[55]እግዚአብሔር ባቢሎንን ያጠፋታል፤
ታላቅ ጩኸቷንም ጸጥ ያደርጋል።
ሞገዳቸው እንደ ታላቅ ውሃ ይተማል፤
ጩኸታቸውም ያስተጋባል።
[56]በባቢሎን ላይ አጥፊ ይመጣል፤
ጦረኞቿ ይማረካሉ፤
ቀስታቸውም ይሰበራል፤
እግዚአብሔር ግፍን የሚበቀል፣
ተገቢውንም ሁሉ የሚከፍል ስምሳክ
ነውና።
[57]ባለ ሥልጣኖቿንና ጥበበኞቿን፣
ገዦቿንና መኳንንቷን፣ ጦረኞቿንም
አሰክራለሁ፤
ለዘላለም ይተኛሉ፤ አይነቁምም፤"
ይላል ስሙ የሰራዊት ጌታ
እግዚአብሔር የሆነው ንጉሥ።

[58]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"ወፍራሙ የባቢሎን ቅጥር ፈጽሞ
ይፈርሳል፤
ከፍ ያሉት ደጆቿም በእሳት
ይቃጠላሉ፤
ሰዎቹ በከንቱ ይደክማሉ፤
የሕዝቡም ልፋት ለእሳት ይሆናል።"

[59]የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ በነገሠ በአራተኛው ዓመት፣ የንጉሡ የግቢ አስከልካይ የነበረው የመሕሤያ ልጅ የኔርያ ልጅ ሠራያ ከንጉሡ ጋር ወደ ባቢሎን በሄደ ጊዜ፣ ነቢዩ ኤርምያስ የሰጠው መልእክት ይህ ነው።

51፥53 ቍ48፤ዘፍ 11፥4፤ኢዮ15፥21፤ ኢሳ14፥13-14
51፥54 ኢዮ24፥12፤ ኤር50፥22
51፥55 መዝ18፥4፤ ኢሳ25፥5
51፥56 ቍ6:48፤ ዘፍ4፥24፤ዘዳ32፥41፤ ኢዮ15፥21፤መዝ 46፥9፤94፥1-2፤ዕብ 2፥8
51፥57 ቍ23:39፤ ኢዮ5፥13፤መዝ76፥5 ፤ኢሳ6፥5፤21፥5፤ኤር 25፥27
51፥58 ቍ44:64፤ 2ነገ25፥4፤ኢሳ15፥1 ፤13፥2፤47፥13:14
51፥59 ኤር28፥1፤ 36፥4፤52፥1
51፥60 ዘፀ 17፥14፤ ኤር30፥2፤ 36፥2
51፥62 ኢሳ13፥20፤ ኤር9፥11፤50፥13
51፥63 ዘፍ2፥14
51፥64 ቍ58፤ኢዮ 31፥40፤መዝ26፥21፤ 28፥19፤ ሩት 18፥21
52፥1 ዘኍ 33፥20፤ ኢሱ 10፥29፤ 2ነገ 8፥22፤ 24፥17
52፥2 ኤር 36፥30
52፥3 ዘፍ 4፥14፤ ዘፀ 33፥15፤ ኢሳ 3፥1፤ሕዝ17፥12-16
52፥4 ኤር 6፥6፤ 34፥1፤ሕዝ24፥1-2፤ ዘካ 8፥19

[60]ኤርምያስ ስለ ባቢሎን ጽፎ ያስቀመጠውን ሁሉ፣ በባቢሎን ላይ የሚመጣውን ጥፋት ሁሉ በብራና ጥቅልል ላይ ጻፈው፤ [61]ለሠራያም እንዲህ አለው፤ "ባቢሎን በደረስህ ጊዜ፣ ይህን ቃል ሁሉ ድምፅህን ከፍ አድርገህ ማንበብ አትዘንጋ [62]እንዲህም በል፤ 'እግዚአብሔር ሆይ፤ ይህችን ስፍራ ሰውም ሆነ እንስሳ እስከማይኖርባት ድረስ ለዘላለም ባድማ አደርጋታለሁ ብለሃል።' [63]ይህን ብራና አንብበህ ከጨረስህ በኋላ፣ ድንጋይ አስረህበት ኤፍራጥስ ወንዝ ውስጥ ጣለው፤ [64]እንዲህም በል፤ 'ባቢሎንም እኔ ከማመጣባት ጥፋት የተነሣ፣ እንደዚሁ ትሰጥማለች፤ ከእንግዲህም አትነሣም፤ ሕዝቧም ይወድቃል።' "

የኤርምያስ ቃል እዚህ ላይ ይፈጸማል።

## የኢየሩሳሌም መውደቅ

52፥1-3 ተጓ ምብ-2ነገ24፥18-20፤2ዜና36፥11-16
52፥4-16 ተጓ ምብ-ኤር39፥1-10
52፥4-21 ተጓ ምብ-2ነገ25፥1-21፤2ዜና36፥17-20

**52** ሴዴቅያስ ሲነግሥ ዕድሜው ሃያ አንድ ዓመት ነበረ፤ በኢየሩሳሌም ዐሥራ አንድ ዓመት ነገሠ፤ የእናቱም ስም አሚጣል ሲሆን፣ እርሷም የሊብና ሰው የኤርምያስ ልጅ ነበረች። [2]ሴዴቅያስም ኢዮአቄም እንዳደረገው ሁሉ፣ በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ነገር አደረገ። [3]እግዚአብሔር በኢየሩሳሌምና በይሁዳ ላይ ይህን ሁሉ ያደረሰውንና በመጨረሻም ከፊቱ ያስወገዳቸው ከቍጣው የተነሣ ነበር።

ሴዴቅያስም በባቢሎን ንጉሥ ላይ ዐመፀ። [4]ስለዚህ ሴዴቅያስ በነገሠ በዘጠነኛው ዓመት በዐሥረኛው ወር፣ ከወሩም በዐሥረኛው ቀን፣ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ሰራዊቱን ሁሉ አስከትቶ በኢየሩሳሌም ላይ ዘመተ፤ ከተማይቱንም ከበባት፤ በዙሪያ

[1]54 ወይም ከለዳውያን

51፥53 *ወደ ሰማይ ብትወጣም፣* ከኢዮ 20፥6 ጋር ያነጻጽሩ። ዘፍ11፥4 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም14፥13-15 ይመ። *አጥፊዎችን፤* ቍ48 እና 56 ይመ።

*51፥54፤* 50፥46 ይመ። *የታላቅ ጥፋት፤* የ4፥6 ማብ ይመ።

51፥55 *ሞገዳቸው፤* የቍ42 ማብ ይመ። *ታላቅ ውሃ፤* የመዝ32፥6 ማብ ይመ።

51፥56 *ተገቢውንም ሁሉ የሚከፍል አምላክ፤* የቍ24 ማብ ይመ።

51፥57 *አሰክራለሁ፤* ቍ39 ይመ፤ እንዲሁም የ25፥15-16:26 ማብ ይመ። *ባለ ሥልጣኖቿንና ጥበበኞቿን፤* 50፥35 ይመ። *ንጉሥ፤* የ46፥18 ማብ ይመ። እውነተኛው ንጉሥ ጌታ እንጂ፣ ቤል/ማርዱክ አይደለም (50፥2 እና ማብ ይመ)።

51፥58 *ወፍራሙ የባቢሎን ቅጥር፤* የቍ44 ማብ ይመ። *ከፍ ያሉት ደጆቿም፣* ስመ ጥር የሆነው የኢሽታር ደጃፍ ቁመቱ ሃያ ክንድ ገደማ ነበር። *የሕዝቡም ልፋት ... ለእሳት ይሆናል፤* በዕን2፥13 ላይ ከተነገረው ጋር ተመሳሳይ ነው።

*51፥59-64፤* ባጠቃላይ ለመጽሐፉና በተናጠል ደግሞ በባቢሎን ላይ ለተነገረው ትንቢት መደምደሚያ።

51፥59 *የግቢ አስከልካይ፤* ቃል በቃል ሲተረጐም "የሚሰፈርበት ቦታ ሹም" ማለት ነው። ጉዞ በሚደረግበት ጊዜ ሕዝቡ መቼና የት ማደር እንዳለባቸው የሚወስን ሰው ነው። *የኔርያ ልጅ ሠራያ፤* "የኔርያ ልጅ የሠራያ ነው" የሚል ጽሑፍ የተቀረጸበት ማኅተም፣ እዚህ ላይ የተጠቀሰውን ሰው የሚያመለክት ስለመሆኑ ጥርጣሬ የለም። ይህ ሰው የኤርምያስ ጸሓፊ የባሮክ ወንድም ነበር (32፥12 ይመ)። *የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ ... በአራተኛው ዓመት፤* ዘመኑ 593 ዓ.ቅ.ክ ነው። ሴዴቅያስ ወደ ባቢሎን ተጠርቶ የሄደው ንጉሥ ናቡከደነፆር ለጥያቄ ፈልጎት ሳይሆን አይቀርም (የ27፥3 ማብ ይመ)።

51፥60 *በብራና ጥቅልል፤* ዘፀ17፥14 ይመ። *ስለ ባቢሎን ጽፎ ያስቀመጠውን ሁሉ፤* የ50፥2-51፥58 ትንቢት ይሆናል (የ50፥1 ማብ ይመ)።

*51፥62፤ ብለሃል፤* ቍ26 ይመ።

51፥64 *የኤርምያስ ቃል እዚህ ላይ ይፈጸማል፤* ይህ ትንቢተ ኤርምያስን አሰባስቦ ላዘጋጀው ሰው የተሰጠ ማስታወሻ ነው (48፥47 ይመ)።

*52፥1-27:31-34፤* ከነገ24፥18-25፥21:27-30 ጋር ተጓዳኝ ነው (የዚያኑ ማብ ይመ)። (52፥4-7: በ39፥1-10 ላይ በአጭሩ ቀርቦአል፤ የዚያኑ ማብ ይመ)። መጽሐፈ ነገሥትን የጻፈው ወይም የጻፉ ሰዎችና ተጨማሪውን የትንቢተ ኤርምያስ ክፍል የጻፈው ሰው ምንጫቸው አንድ መሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም፤ ተጨማሪውን ክፍል የጻፈው ባሮክ ነው፤ በጥቂት ምንባቦች ኤርምያስ ከነገሥት ይልቅ የተሟላ ሆኖ ይታያል (ቍ10-11፤ ከ2ነገ 25፥7፤ ቍ15፤ ከ2ነገ25፥11፤ቍ19-23ን ከ2ነገ25፥15-17፤ ቍ31ን ከ2ነገ25፥30 ጋር ያነጻጽሩ)።

52፥1 *ኤርምያስ፤* ይህ ነቢዩ ኤርምያስ አይደለም።

ውም የዐፈር ድልድል ሠሩ:: 5 ከተማዪቱም እስከ ንጉሡ እስከ ሴዴቅያስ ዐሥራ አንደኛ ዘመነ መንግሥት ተከባ ነበር::

6 በአራተኛው ወር በዘጠነኛው ቀን በከተ ማይቱ ራብ ጸንቶ ስለ ነበር ሕዝቡ የሚበ ላውን አጣ፤ 7 የከተማዪቱም ቅጥር ተነደለ፤ ሰራዊቱም ሁሉ ኰብልሎ ሄደ:: ባቢ ሎናውያን[ሶ] በከተማዪቱ ዙሪያ ቢኖሩም፣ በን ጉሡ የአትክልት ስፍራ አጠገብ በሁለት ቅጥሮች መካከል ባለው በር በሌሊት ከተ ማዪቱን ጥለው ሸሹ፤ ወደ ዓረባም[ጀ] አመሩ:: 8 የባቢሎናውያንም[ገ] ሰራዊት ንጉሥ ሴዴ ቅያስን ተከታትሎ በማሳደድ በኢያሪኮ ሜዳ ደረሱበት፤ ወታደሮቹም ሁሉ ከእርሱ ተለ ይተው ተበታትነው ሳለ፣ ንጉሡን ያዙት::

9 እርሱም በሐማት ምድር በሪብላ ወደ ነበረው ወደ ባቢሎንም ንጉሥ ተወሰደ፤ የባቢሎን ንጉሥ በዚያ ፈረደበት:: 10 በሪብ ላም የባቢሎን ንጉሥ፣ የሴዴቅያስን ወንዶች ልጆች በአባታቸው ፊት ዐረዳቸው፤ የይሁ ዳንም ባለሥልጣኖች ሁሉ ገደላቸው፤ 11 የሴ ዴቅያስንም ዐይኖች አወጣ፤ በናስ ሰን ሰለትም አስሮ ወደ ባቢሎን ወሰደው፤ በዚ ያም እስከ ዕለተ ሞቱ በእስር ቤት አቈየው::

12 የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በነገሠ በዐ ሥራ ዘጠነኛው ዓመት በአምስተኛው ወር፤ ከወሩም በዐሥረኛው ቀን፣ የባቢሎን ንጉሥ ባለሟል የክብር ዘበኞች አዛዥ የነበረው ናቡዘረዳን ወደ ኢየሩሳሌም መጣ:: 13 *የእ ግዚአብሔርን* ቤተ መቅደስና የንጉሡን ቤተ መንግሥት እንዲሁም በኢየሩሳሌም የነበሩትን ቤቶች ሁሉ በእሳት አቃጠለ፤ ሌሎች ትልልቅ ሕንጻዎችንም በእሳት አወ ደመ:: 14 በክብር ዘበኞቹ አዛዥ ሥር የነበሩት የባቢሎናውያን ሰራዊት ሁሉ በኢየሩሳ ሌም ዙሪያ ያለውን ቅጥር በሙሉ አፈረሱ:: 15 የዘቦቹ አዛዥ ናቡዘረዳን አንዳንድ ድኾ ችንና በከተማይቱ የቀረውን ሕዝብ፣ የእጅ ጥበብ ያላቸውንና[መ] ሸሽተው ወደ ባቢሎን ንጉሥ የተጠጉትን አፈለሳቸው:: 16 ነገር ግን የክብር ዘበኞቹ አዛዥ ናቡዘረዳን ሌሎች የምድሪቱን ድኾች ወይን ተካዮችና ዐራሾች እንዲሆኑ አስቀራቸው::

17 ባቢሎናውያን *በእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ የነበሩትን የናስ ዐምዶች፣ ተንቀሳ ቃሽ ማስቀመጫዎችንና ከናስ የተሠራውን የውሃ ገንዳ ሰባበሩ፤ ናሱንም ሁሉ ወደ ባቢ ሎን ይዘው ሄዱ:: 18 ከእነዚህም ሌላ ምን ቸቶቹን፣ መጫሪያዎቹን፣ መኰስተሪያዎቹን፣ ወጭቶችን፣ ጭልፋዎቹንና ለቤተ መቅደስ አገልግሎት የሚውሉትን የናስ ዕቃዎች በሙሉ ወሰዱ:: 19 የክብር ዘበኞቹ አዛዥ ከን ጹሕ ወርቅና ከንጹሕ ብር የተሠሩትን ዕቃ ዎች ሁሉ ጐድጓዳ ሳሕኖችን ጥናዎችን፣ ወጭቶችን፣ ምንቸቶችን፣ መቅረዞችን፣ ጭልፋዎችንና ለመጠጥ ቍርባን ማቅረቢያ የሚሆኑ ወጭቶችን ይዞ ሄደ::

20 ንጉሥ ሰሎሞን *ለእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ከናስ ያሠራቸው:- ሁለቱ ዐምዶች፣ ትልቁ የውሃ ገንዳ፣ ከሥሩ ያሉት ዐሥራ ሁለት ወይፈኖችና ተንቀሳቃሽ ማስቀመ ጫዎች ክብደታቸው ሚዛን ከሚችለው በላይ ነበር:: 21 እያንዳንዱም ዐምድ ከፍታው ዐሥራ ስምንት ክንድ ዙሪያ ክቡም[ጨ] ዐሥራ ሁለት ክንድ ነበረ፤ ውስጡ ክፍት ስለ ሆነ የእያንዳንዱ ከንፈር ውፍረት አራት ባት ነበረ:: 22 በአንዱ ዐምድ ዐናት ላይ ያለው የናስ ጕልላት ቁመት አምስት ክንድ[ሰ] ሲሆን፣ ዙሪያውንም ሁሉ የሮማን ቅርጽ ባላቸው የናስ ጌጣ ጌጦች የተዋበ ነበር፤ ሌላውም ዐ ምድ የሮማኑን ጌጣጌጥ ጨምሮ ከዚሁ ጋር አንድ ዐይነት ነበር:: 23 ዘጠና ስድስቱ ሮማኖች ከጐን በቀላሉ የሚታዩ ሲሆኑ፣ በአጠቃላይ በዙሪያው ካለው ጌጥ በላይ ያለው የሮማኖች ቍጥር አንድ መቶ ነበር::

24 የክብር ዘበኞቹ አዛዥ የካህናት አለቃ የነበረውን ሠራያን፣ ምክትሉንም ካህን ሶፎ ንያስንና ሦስቱን በር ጠባቂዎች አስሮ ወሰ ዳቸው፤ 25 በከተማው ውስጥ ከቀሩትም ሕዝብ፣ የተዋጊዎቹ ኀላፊ የነበረውን መኰንን፣ ሰባቱን የንጉሡን አማካሪዎች ከአገሬው ሕዝብ ወታደር የሚመለምለውን መኰንን ጸሓ ፊና በከተማው ውስጥ የተገኙትን ሌሎች ስድሳ ሰዎች ወሰደ:: 26 የክብር ዘበኞቹ አዛዥ ናቡዘረዳን እነዚህን ሁሉ ይዞ የባቢ ሎን ንጉሥ ወደ ነበረበት ወደ ሪብላ አመ ጣቸው:: 27 ንጉሡም በሐማት ምድር በነበረ ችው በሪብላ ፈጃቸው::

ይሁዳም በዚህ ሁኔታ ከምድሯ በምርኮ ተወሰደች:: 28 ናቡከደነፆር ማርኮ የወሰደው ሕዝብ ቍጥር እንደሚከተለው ነው:-

በነገሠ በሰባተኛው ዓመት፣ ሦስት ሺህ ሃያ ሦስት አይሁድ፤ 29 ናቡከደነፆር በነገሠ በዐሥራ ስምንተኛው ዓመት፣ ስምንት መቶ

52፥6 ዘሌ26፥26፤ ኢሳ3፥1፤ ሰቆ1፥11
52፥7 ሰቆ4፥19
52፥9 ዘኍ13፥21፤ 34፥11፤ኤር21፥7፤ 32፥4
52፥10 ኤር22፥30
52፥11 ኤር34፥4 ፤ሕዝ12፥13፤17፥16
52፥12 ቍ26፤ዘካ 7፥5፤8፥19
52፥13 ዘዳ13፥16፤ 29፥24፤2ዜና36፥19 ፤መዝ74፥8፤79፥1፤ ኤር19፥13፤ሰቆ2፥6 ሚክ3፥12፤
52፥14 ነህ1፥3፤ ሰቆ 2፥8
52፥15 2ነገ24፥1፤ ኤር1፥3፤38፥19
52፥16 ኤር40፥6
52፥17 1ነገ7፥15፡ 27-37፤27፥19-22
52፥18 ዘፀ27፥3፤ ዘኍ4፥14፤1ነገ7፥45
52፥19 ዘፀ25፥29፤ ዘሌ10፥1፤ዘኍ3፥31 ፤4፥7፤1ነገ7፥50፤ዕዝ 1፥7፤ዳን5፥2
52፥20 1ነገ7፥25፡ 47
52፥21 1ነገ7፥15
52፥22 ዘፀ28፥33፤ 1ነገ7፥16
52፥23 ቍ17፤1ነገ 7፥20፤ ኤር 27፥19
52፥24 2ነገ 12፥9፤ 25፥18፤ ኤር 37፥3
52፥25 ኤር 36፥10
52፥26 ቍ12
52፥27 ዘኍ 34፥11፤ ኤር 20፥4
52፥28 ዘዳ 28፥36፤ 2ዜና 36፥20፤ ነህ 1፥2

ሶ7 *ወይም ከለዳውያን፤ ቍ 17 ይመ::*
ጀ7 *ወይም የርዳኖስ ሸለቆ*
ገ8 *ወይም ከለዳውያን፤ ቍ 14 ይመ::*
መ15 *ወይም ተራው ሕዝብ*

52፥12 *በዐሥረኛው ቀን፤* የዚህ ተጓዳኝ 2ነገ25፥8 በሰባተ ኛው ቀን ይለዋል:: ከሁለቱ ቍጥሮች አንዱ ቅጅውን በገለበጠው ሰው የተፈጸመ ስሕተት ነው፤ ነገር ግን ስሕተቱ የት ላይ እንደ ሆነ ለይተን ማመልከት አንችልም (ቍ22:25:31 ይመ)::

*52፥18-19፤* 1ነገ7፥40:45:50 ይመ::

52፥20 *ዐሥራ ሁለት ወይፈኖችና፤* የ2ዜና4፥4 ማብ ይመ::

*52፥21-23፤* የ1ነገ7፥15-22 ማብ ይመ::

52፥22 *አምስት፤* በ2ነገ25፥17 ላይ የሚገኘው ተጓዳኝ ጽሑፍ "ሦስት" ያደርገዋል:: ምናልባትም ይህ ስሕተት ሊከሠት የቻለው ከአንዱ ወደ ሌላው በሚገለበጥበት ጊዜ ሳይሆን አይቀርም::

52፥25 *ሰባቱን፤* በ2ነገ25፥19 ላይ "አምስት" ይለዋል:: የቍ12ን ማብ ይመ::

52፥28 *በሰባተኛው ዓመት፤* ናቡከደነፆር ከነገሠበት ጊዜ ጀምሮ በመቍጠር (ቍ29-30 ይመ)፤ ዘመኑ 597 ዓ.ቅ.ክ ነው:: ሦስት ሺህ ሃያ ሦስት፤ ምናልባትም ለዐቅመ አዳም የደረሱትን የሚጨምር ሊሆን ይችላል፤ ከዚሁ ጋር ተመሳሳይ የሆነው በ2ነገ 24፥14:16 የተጻፈው ቍጥር እጅግ ከፍ ያለ ነውና::

52፥29 *በዐሥራ ስምንተኛው ዓመት፤* ዘመኑ 586 ዓ.ቅ.ክ

ሠላሳ ሁለት ሰዎች ከኢየሩሳሌም፤
[30]ናቡከደነፆር በነገሠ በሃያ ሦስተኛው ዓመት፣ የክብር ዘበኞች አዛዥ ናቡዘረዳን ሰባት መቶ አርባ አምስት አይሁድ ማርኮ ወሰደ አል፤ በአጠቃላይ አራት ሺህ ስድስት መቶ ሰዎች ነበሩ።

### የዮአኪን መፈታት

[31]የይሁዳ ንጉሥ ዮአኪን በተማረከ በሠላሳ ሰባተኛው ዓመት፣ ዮርማሮዴክ* በባቢሎን ነገሠ፤ በዚሁ ዓመት፣ በዐሥራ ሁለተኛው ወር ከወሩም በሃያ አምስተኛው ቀን የይሁዳን ንጉሥ ዮአኪንን አሰበው፤ ከእስር ቤትም አወጣው፤ [32]በመልካምም ቃል አናገረው፤ ከእርሱም ጋር በባቢሎን በምርኮ ከነበሩት ነገሥታት ይልቅ ከፍ ባለ የክብር ቦታ አስቀመጠው። [33]ዮአኪንም እስር ቤት ለብሶት የነበረውን ልብሱን አውልቆ ጣለ፤ በቀረውም የሕይወቱ ዘመን ሁሉ ከንጉሡ ማእድ ይበላ ነበር። [34]የባቢሎንም ንጉሥ፣ ዮአኪን እስኪሞት ድረስ፣ በሕይወት ዘመኑ ሁሉ ሳያቋርጥ በየዕለቱ ቀለቡን ይሰጠው ነበር።

52፥30 ኤር 13፥19፤ 43፥3
52፥31 2ዜና 36፥9
52፥33 2ዜና 9፥7
52፥34 2ሳሙ 9፥10

ₒ21 ከፍታው 27 ጫማ (8.1 ሜትር) እና ዙሪያ ክቡ 18 ጫማ (5.4 ሜትር) ገደማ ነው።
*22 7½ ጫማ (2.3 ሜትር) ገደማ ነው።
*31 እንዲሁም *ኢሜልማርዱክ* ተብሎ ይጠራል።

ነው። ይህ ቍጥር በቍ12 ላይ "ዐሥራ ዘጠኝ ዓመት" ተብሎ ተጠቅሶአል። የአቈጣጠር ልዩነት ሊከሠት የቻለው የነገሥታቱን የአገዛዝ ዘመን ልዩነት ከመከተል የተነሣ ነው (የዳን1፥1 ማብ ይመ)።

*52፥30፤* ዘመኑ 581 ዓ.ቅ.ክ ነው። *ናቡዘረዳን ... ማርኮ ወስዶአል፤* ይህ እርምጃ የተወሰደው (1) ሌላ ዐመፅ እንዳይነሣ ለማምከን (ቍ3)፣ ወይም (2) በጎዶልያስ ላይ የተፈጸመውን ግድያ ለመቀበል ሳይሆን አይቀርም (41፥1-3 ይመ)።

*52፥31-34፤* በ2ነገ25፥27-30 ላይ የተጻፈውን በአብዛኛው ደግሞታል (የዚያኑ ማብ ይመ)። ኤርምያስም ሆነ መጽሐፈ ነገሥት ታሪኩን የሚደመድሙት እንዲህ ባለ ደስ በሚያሰኝ ሁኔታ ነው።

52፥31 *በሃያ አምስተኛው፤* የዚህ ተጓዳኝ የሆነው የ2ነገ 25፥27 ምንባብ ግን "ሃያ ሰባተኛው" ይላል። የቍ12 ማብ ይመ።

52፥34 *እስኪሞት ድረስ፤* ቍ11 ይመ። ይህ ሐረግ በ2ነገ ላይ በሚገኙት ተጓዳኝ ቍጥሮች ውስጥ በየትኛውም ምክንያት ስለማይታይ፣ ምናልባት ዋና ትኵረቱ እስከ ዕለተ ሞቱ ታስሮ በቈየው በሴዴቅያስና (ቍ11) ከእስር ቤት ተለቆ በባቢሎን ነገሥታት ዘንድ ሞገስ ባገኘውና እስከ ሞትም ድረስ በነጻነት መኖር በቻለው በኢዮአቄም መካከል ያለውን ልዩነት በጕልሕ ለማሳየት ሳይሆን አይቀርም።

# ሰቆቃወ ኤርምያስ

## መግቢያ

### አሰያየሙ

የመጽሐፉ ስም በዕብራይስጥ "ኤካህ"("እንዴት ... ")የሚል ሲሆን ይህም የተወሰደው በመጽሐፉ መግቢያ ላይ ከሚገኘው የመጀመሪያ ቃል ነው፤ ይህ ቃል በ1፥1፤ 2፥1፤4፥1 ላይ ይገኛል:: ይሁን እንጂ መጽሐፉ በውስጡ ካካተተው ሐሳብ በመነሣት አይሁድ በትውፊታቸው፣ "ሰቆቃወ ኤርምያስ" ብለውታል:: ይህ ስም በግሪኩና በላቲኑም ትርጒሞች ላይ ይገኛል::

### ጸሓፊውና የተጻፈበት ጊዜ

የዚህ መጽሐፍ ጸሓፊ ማን እንደ ሆነ በትክክል ባይታወቅም፣ በአይሁድና በክርስትና ትውፊት መሠረት ይህን መጽሐፍ የጻፈው ኤርምያስ ነው:: ለዚህ በከፊል ምክንያት የሆነው በ2ዜና 35፥25 ላይ የቀረበው ሐሳብ ነው፤ ይህ ማለት ግን በጥቅሱ ላይ የተገለጸው "የልቅሶ ግጥም" የሰቆቃወ ኤርምያስ ነው ማለት አይደለም:: በሌላ በኩል ደግሞ ምክንያት ሆኖ የቀረበው በኤር 7፥29፤8፥21፤9፥1:10:20 የተጠቀሱት ዐውዶች በሰቆቃወ ኤርምያስ ከተጠቀሱት ዐውዶች ጋር የቃላት አመራረጥና የአጻጻፍ ስልታቸው ተመሳሳይ መሆኑ ነው:: ከዚህ ሁሉ በላይ ጸሓፊው ኤርምያስ መሆኑን ለማረጋገጥ የሚቀርበው ሐሳብ፣ በ586 ዓ.ቅ.ክ. በኢየሩሳሌም ላይ ለወረደው የእግዚአብሔር ፍርድ ራሱ ኤርምያስ የዐይን ምስክር መሆኑና ሁኔታውን በግልፅ መጻፍ የሚችል እርሱ ብቻ መሆኑ ነው:: ሰቆቃወ ኤርምያስ የሥቃዩን ደመና ከከተማዪቱና ከቤተ መቅደሱ መደምሰስ እንዲሁም ከሃይማኖት ሥርዐት መፈራረስና ከይሁዳ ሕዝብ ተማርኮ መሄድ ጋር አያይዞ ስሜትን በሚነካ መንገድ ይገልጻል::

ሰቆቃወ ኤርምያስ የተጻፈበት ጊዜ ቀደም ባለው ዘመን ነው ተብሎ ከተገመተ በ586 ዓ.ቅ.ክ. ሲሆን፣ ዘግየት ብሎ ነው ከተባለ ደግሞ ቤተ መቅደሱ እንደ ገና ተሠርቶ በተመረቀበት በ516 ዓ.ቅ.ክ. ላይ ይሆናል:: ከሰቆቃወ ኤርምያስ መጽሐፍ ጋር የተዛመደ ጽሑፍ ዘመኑን ቀደም ያደርገዋል፤ ይህም በ575 ዓ.ቅ.ክ. በፊት መሆኑ ነው::

### ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ

ሰቆቃወ ኤርምያስ አምስት ምዕራፎች ያሉት ሆኖ በቅኔ መልክ የቀረበ መጽሐፍ ነው:: ሥልሳ ስድስት ቍጥሮች ካሉት ከምዕራፍ ሦስት በስተቀር እያንዳንዱ የልቅሶ ግጥም ሃያ ሁለት ቍጥሮች አሉት፤ እያንዳንዱም ቍጥር የዕብራይስጡን የሆህያት ቅደም ተከተል ጠብቆ የተጻፈ ነው:: ሦስቱ የመጀመሪያዎቹ ምዕራፎች ርዝመታቸው እኩል ነው:: ከ1፥7 በስተቀር በእያንዳንዱ የመጀመሪያና የሁለተኛ ምዕራፍ ጥቅስ ውስጥ ሦስት ሦስት የዕብራይስጥ ስንኞች ሲኖሩ፣ ስድሳ ሥልሳ ቍጥሮች ባሉት በሦስተኛው ምዕራፍ አንዳንድ ስንኝ አለ:: ሁለት ሁለት ስንኞች ያሉት አራተኛው ምዕራፍና አንድ አንድ ስንኝ ያለው አምስተኛው ምዕራፍ አጫጭሮች ናቸው:: የልቅሶ ግጥሞቹ ስሜትን የሚነኩ ቢሆኑም፣ በሆሂያት ቅደም ተከተል መዋቀራቸው በጥንቃቄ ተጠንተው መዘጋጀታቸውን ያመለክታል::

### መሪ ሐሳቡና ትምህርተ መለኮቱ

ሰቆቃወ ኤርምያስ የግለ ሰብንም ሆነ የኅብረተ ሰብን የልቅሶ ግጥም የያዘ ብቸኛ የብሉይ ኪዳን መጽሐፍ አይደለም:: ከመዝሙረ ዳዊትም በቅኔ መልክ የቀረቡ አያሌ የልቅሶ ግጥሞችን መጥቀስ ይቻላል፤ እንዲሁም ከትንቢተ ሐጌ በስተቀር ከእያንዳንዱ የትንቢት መጽሐፍ አንድ ወይም ብዙ የልቅሶ ግጥሞችን ምሳሌ አድርጎ መጥቀስ ይቻላል:: ይሁን እንጂ ሙሉ በሙሉ የልቅሶ ግጥምን የያዘ መጽሐፍ ሰቆቃወ ኤርምያስ ብቻ ነው::

በ586 ዓ.ቅ.ክ የተፈጸመውን የኢየሩሳሌምን መጥፋት በተመለከተ ተጽፎ በሰቆቃወ ኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ የሚገኘው የልቅሶ ግጥም በትውፊት ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ከሆኑ ከሱሜራውያን ጽሑፎች ማለት፣ "ስለ ዑር መደምሰስ የተደረገ የልቅሶ እንጕርጕሮ"፣ "በሱመርና በዑር መደምሰስ ላይ የተደረገ የልቅሶ ግጥም" እና "በኒፑር መደምሰስ ላይ የተደረገ የልቅሶ ግጥም" ከተባሉት ጋር ይመደባል:: የአይሁድ እምነት ተከታዮች በ586 ዓ.ቅ.ክ የተደመሰሰውን የሰሎሞን ቤተ መቅደስ በያመቱ በሚያስቡበት በአቢብ ወር በዘጠነኛው ቀን በዚያው ዕለት፣ እንዲሁም በ70 ዓ.ም. የተደመሰሰውን የሄሮድስ ቤተ መቅደስ በያመቱ በሚያስቡበት ቀን ድምፃቸውን ከፍ አድርገው ሰቆቃወ ኤርምያስን ከዳር እስከ ዳር ማንበባቸው የተለመደ ነው:: ብዙዎችም በጥንታዊቱ የኢየሩሳሌም ከተማ ውስጥ ወደሚገኘው የምዕራቡ ግንብ ወይም "የልቅሶ ግንብ" እየተባለ ወደሚጠራው ስፍራ በየሳምንቱ በመሄድ ሰቆቃወ ኤርምያስን ያነቡታል:: በተጨማሪም መጽሐፉ በነባሩ ወይም በጥንቱ ትውፊት የሮማ ካቶሊክ ሥርዐተ ጸሎት ውስጥ ስፍራ ተሰጥቶት በተለይም፣ "በሰሙነ ሕማማት በሕማማት ሰሞን" በመጨረሻዎቹ ሦስት ቀናት ውስጥ ይነበባል::

ይህ በኋለኛው ትውፊት ላይ የተገለጸው ሥርዐተ ጸሎት የሰቆቃወ ኤርምያስ መጽሐፍ ስለ ኢየሩሳሌም መደምሰስ ብቻ የሚናገር ሳይሆን፣ ጥልቅ የሆነ ነገረ መለኮታዊ ትምህርት የሚገኝበት እንደ ሆነም ያመለክታል:: ይሁን እንጂ በ586 ዓ.ቅ.ክ ላይ የነበረው አስደንጋጭ ሁኔታ በእርግጥም የሚዘነጋ አይደለም:: ከዚህ የተነሣም:-

(1) ጅምላ ጭፍጨፋና ግድያ በነገሥታት (2፥6:9፤4፥20)፣ በመሳፍንት (1፥6፤2፥2:9፤4፥7-8:5፥12) በሽ

ማግሌዎች (1፥19፤2፥10፤4፥16፤5፥12)፣ በካህናት (1፥4፤19፤2፥6:20፤4፥16)፣ በነቢያት (2፥9:20)፣በተራው ሕዝብና (2፥10-12:3፥48፤4፥6) በሌላው ሁሉ ላይ ደርሶአል።

(2) የተራቡ እናቶች ልጆቻቸውን እስከመብላት ደርሰዋል (2፥20:4፥10)።

(3) እንደ አበባ ፈክተው ይታዩ የነበሩት የይሁዳ ልጆች ሐፍረትን፣ ውርደትን ተጐናጽፈው እንደ ከብት እየተነዱ በምርኮ ሄደዋል (1፥3:18)።

(4) እጅግ ከፍ ባለ ሥነ ሥርዐት ይፈጸም ወይም ይከናወን የነበረው በዓልና አምልኮ አብቅቶለታል (1፥4:10)።

ከዚህም ሌላ ከፍ ያለ ግምት ሊሰጣቸው የሚገባቸው ነገሮችም እንዲሁ ደርሰዋል ተፈጽመዋልም።

የሰቆቃወ ኤርምያስ ጸሐፊ እግዚአብሔር አምላካዊውን ቅጣት ለመፈጸም ባቢሎናውያንን መምቻ በትሩ አድርጎ የተጠቀመባቸው መሣሪያዎች መሆናቸውን በሚገባ ተረድቶአል፤ የራሱን ከተማና ቤተ መቅደስ ያጠፋውም ራሱ እግዚአብሔር መሆኑን ደጋግሞ ተናግሮአል (1፥12-15:2፥1-8:17:22:4፥11)። ወይም እግዚአብሔር ይህን ያለምክንያት እንዲሁ በዘፈቀደ ያመጣው ሳይሆን፣ በድፍረት በአምላክ ላይ የተፈጸመ ኀጢአትና የተሰጠውን ቃል ኪዳን በማፍረስ የተፈጸመ ዐመፅ ለሕዝቡ ዋይታ ዋነኛው ምክንያት መሆኑን ገልጾአል (1፥5:8-9:4፥13:5፥7:16)። ማልቀስ (1፥16:2፥11:18:3፥48-51) ተገቢ ቢሆንም እንዲሁም ጠላት በሚያደርሰው ጥፋት ጩኸ ጩኸ ቢያሰኝም (1፥22:3፥59-66) በፍርድ ጊዜ ተገቢውን ምላሽ መስጠትና ከልብ የሆነ ስብራት (3፥40-42) የሚጠበቅ ነው። በልቅሶ ግጥም የሚጀምረው መጽሐፍ በትክክለኛ ንስሓ ተፈጽሞአል (5፥21-22)።

የሰቆቃወ ኤርምያስ ሥነ መለኮት ከመጨረሻው ከፍተኛ ደረጃ ላይ ደርሶ የምናየው በመጽሐፉ መካከል ላይ ሲሆን፣ ይህም በእግዚአብሔር መልካምነት ላይ ያተኰረ ነው። እግዚአብሔር የተስፋ፣ (3፥21:24-25)፣ የፍቅር (3፥22)፣ የታማኝነት (3፥23)፣ የድነት (3፥26) ጌታና ባለ ቤት ነው። ነገሩ የሚቃረን ቢመስልም እንኳ ለዚህ ሁሉ ማስረጃ የሚሆነው፣ "... ምሕረቱ አያልቅምና፤ ማለዳ ማለዳ አዲስ ነው፤ ታማኝነትህ ብዙ ነው" (3፥22-23) የሚለው ጥቅስ ነው።

**አስተዋፅኦ**

(1) የኢየሩሳሌም መከራና ጥፋት (ም1)

(2) የእግዚአብሔር ቍጣ በሕዝቡ ላይ (ም2)

(3) የይሁዳ ክርክርና መጽናናት መሠረተ ነገር (ም3)

(4) ያለፈው የጽዮን ሁኔታና የአሁኑ ሲነጻጸር (ም4)

(5) የእግዚአብሔር ምሕረት እንዲመጣ ይሁዳ ያቀረበችው ጥያቄ (ም5)

# 1

[አሌፍ] በሕዝብ ተሞልታ የነበረችው
ከተማ፣
እንዴት የተተወች ሆና ቀረች!
በሕዝቦች መካከል ታላቅ የነበረችው፣
እርሷ እንዴት እንደ መበለት ሆነች!
በአውራጃዎች መካከል ልዕልት
የነበረችው፣
አሁን ባሪያ ሆናለች።

[2 ቤት] በሌሊት አምርራ ታለቅሳለች፤
እንባዋ በጉንጮችዋ ላይ ይወርዳል፤
ከወዳጆቿ ሁሉ መካከል ፣
የሚያጽናናት ማንም የለም፤
ባልንጀሮቿ ሁሉ ከድተዋታል፤
ጠላቶቿም ሆነዋል።

[3 ጋሜል] በመከራና በመረገጥ ብዛት
ይሁዳ ተማርካ ሄደች፤
በሕዝቦችም መካከል ተቀመጠች፤
የምታርፍበትንም ስፍራ አጣች፤
በጭንቀቷ መካከል ሳለች፣
አሳዳጆቿ ሁሉ አገኟት።

[4 ዳሌጥ] የጽዮን መንገዶች ያለቅሳሉ፤
በዓላቷን ለማክበር
የሚመጣ የለምና፤
በበሮቿ ሁሉ የሚገባና የሚወጣ የለም፤
ካህናቷ ይቃትታሉ፤
ደናግሏ ክፉኛ አዝነዋል፤
እርሷም በምሬት ትሠቃያለች።

[5 ሄ] ባላጋሮቿ ገዥዎቿ ሆኑ፤
ጠላቶቿ ተመችቶአቸዋል፤
ከኀጢአቷ ብዛት የተነሣ፣
*እግዚአብሔር* ከባድ ሐዘን
አምጥቶባታል።
ልጆቿ በጠላት ፊት ተማርከው፣
ወደ ግዞት ሄደዋል።

[6 ዋው] የጽዮን ሴት ልጅ፣
ግርማ ሞገሷ ሁሉ ተለይቶአታል፤
መሳፍንቶቿ፣
መሰማሪያ እንዳጣ ዋልያ ናቸው፤
በአሳዳጆቻቸው ፊት፣
በድካም ሸሹ።

[7 ዛይ] በተጨነቀችባቸውና በተንከራ
ተተችባቸው ቀናት፣
ኢየሩሳሌም በጥንት ዘመን የነበራትን፣
ሀብት ሁሉ ታስባለች፤
ሕዝቦቿ በጠላት እጅ በወደቁ ጊዜ፣
የረዳት ማንም አልነበረም፤
ጠላቶቿ ተመለከቷት፤
በመፈራረሷም ሣቁ።

[8 ሔት] ኢየሩሳሌም ከባድ ኀጢአት
ሠርታለች፤
ስለዚህም የረከሰች ሆናለች፤
ያከበሯት ሁሉ ናቋት፤
ዕራቍቷን ሆና አይተዋታልና፤
እርሷ ራሷ ታጕረመርማለች፤
ወደ ኋላዋም ዘወር ብላለች።

[9 ጤት] ርኵሰቷ በቀሚሷ ላይ ታየ፤
ወደፊት የሚሆንባትን አላሰበችም፤
አወዳደቋ አስደንጋጭ ሆነ፤
የሚያጽናናትም አልነበረም፤
"*እግዚአብሔር* ሆይ፤ መከራዬን
ተመልከት፤
ጠላት ድል አድርጎአልና!"

[10 ዮድ] በሀብቷ ሁሉ ላይ፣
ጠላት እጁን ዘረጋ፤
ወደ ጉባኤህ እንዳይገቡ፣
የከለከልሀቸው፣

1፥1 ዘሌ26፥43፤1ነገ 4፥21፤ኢሳ3፥26፤ 47፥8፤ ኤር40፥9፤ 42፥2፤ሕዝ5፥5
1፥2 ቍ16፤መዝ 6፥6፤ ኤር3፥1፤ 4፥30፤30፥14፤ ሚክ 7፥5
1፥3 ዘፀ15፥9፤ዘዳ 28፥65፤ኤር13፥19
1፥4 ቍ21፤መዝ 137፥1፤ኢሳ27፥10፤ ኤር9፥11፤ኢዩ 1፥8-13
1፥5 መዝ5፥10፤ 137፥3፤ኢሳ22፥5፤ ኤር10፥20፤30፥15፤3 9፥9፤52፥28-30፤ ሰቆ2፥17
1፥6 ዘሌ26፥36፤ መዝ9፥14፤ኤር13፥18
1፥7 2ነገ14፥16፤ ኤር2፥26፤37፥7፤ሰቆ 4፥17
1፥8 ቍ20፡21፡22፤ መዝ6፥6፤38፥8፤ኤር 2፥22፤13፥22፡26
1፥9 ዘዳ32፥28-29፤ መዝ25፥18፤ኤር13፥ 18፤16፥7፤መክ4፥1፤ ሕዝ24፥13
1፥10 ዘዳ23፥3፤መዝ 74፥7-8፤79፥1፤ኢሳ 64፥11፤ኤር51፥51

[ሀ1] ይህ ምዕራፍ ጥቅሶቹ ተከታታይ ፊደላት ባሉት የዕብራይስጥ ሆሄያት የሚጀምር፣ የመጀመሪያው ወይም የመጨረሻው መሥመር ትርጕም የማይሰጥ ቃል ወይም ዐረፍተ ነገር ያለው ግጥም ነው።

1፥1 *በሕዝብ ተሞልታ፤* ኢሳ1፥21 ይመ። *ተሞልታ ... ታላቅ፤* በዕብራይስጡ ሁለቱም ቃላት አንድ ናቸው። *ከተማ፤* ኢየሩሳሌም ናት። *ከተማ፣ እንዴት የተተወች ሆና ቀረች፤* ከኢየሩሳሌም ውድቀትና ከተከሠተው አሳዛኝ ሁኔታ የተነሣ፣ ኤርምያስ የተፈጠረበትን ጥልቅ ሐዘን ይገልጻል። ቅድስቲቱ ከተማ ልጆቿን እንዳጣች መበለትና ባልንጀሮቿም አሳልፈው እንደሰጧት በሚገልጽ ሰውኛ ዘይቤ ተገልጻለች። *የተተወች ሆና ቀረች፤* ማንም ሊያጽናናት አይችልም። *እንዴት፤* ድንጋጤና ተስፋ መቍረጥ በአንድነት መከሠታቸውን ይገልጻል (2፥1፤ 4፥1-2፤ ኢሳ1፥21፤ ኤር48፥17 ይመ)። *የተተወች ሆና ቀረች!* ዕብራይስጡ ለዚህ ሐረግ አጽንዖት በመስጠት በኤር15፥17 ላይ፣ "ብቻዬን ተቀመጥሁ" ይለዋል። በዚያኛው ላይ ነቢዩ ብቻውን ተቀምጦአል፤ እዚህ ላይ ግን ብቻዋን የተቀመጠችው በእርሱ የተወደደችው ከተማ ናት። *በሕዝቦች መካከል ታላቅ፤* ከኤር 49፥15 ጋር ያነጻጽሩ። *ባሪያ፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ፣ "ተገዶ የሚሠራ" የሚል ትርጕም አለው (ዘፀ1፥11፤ 1ነገ4፥6 ይመ)።

1፥2፤ *በሌሊት፤* 2፥18-19 ይመ። *አምርራ ታለቅሳለች፤* ተመሳሳይ ሁኔታ ደርሶበት ኤርምያስ እንዳለቀሰው ሁሉ ማለት ነው (ኤር13፥17 ይመ)። *ወዳጆቿ ... ባልንጀሮቿ፤* የፖለቲካ አጋሮቿ ማለት ነው (ለምሳሌ ኤር2፥36-37፤27፥3 ይመ)። *የሚያጽናናት ማንም የለም፤* ቍ9፡16-17፡21 ይመ። *ሁሉ ከድተዋታል፤* ቍ19 ይመ፤ እንደ ኤዶምያስና (4፥21-22፤ መዝ 137፥7 ይመ) እንደ አሞን ልጆች ማለት ነው (ኤር40፥14፤ ሕዝ25፥2-3፡6 ይመ)። *ጠላቶቿም ሆነዋል፤* ቍ17 ይመ።

1፥3 *በሕዝቦችም መካከል ... የምታርፍበትንም ስፍራ አጣች፤* ሙሴ በዘዳ28፥65 ላይ አስቀድሞ እንዳስጠነቀቀው ማለት ነው።

1፥4 *ያለቅሳሉ፤* የተተዉ ስለሆነ ማንም አይሄድባቸውም (መሳ 5፥6፤ኢሳ33፥8 እና ማብ ይመ። *በዓላቷን፤* ዘፀ23፥14-17 እና ማብ፤ ዘሌ23፥2 ይመ። *ደናግሏ ክፉኛ አዝነዋል፤* ሙሉ በሙሉ የመሸነፍ ምልክት ነው (ከዘፀ15፥20 እና ማብ፤ ከመሳ 21፥19፡21፤ ከመዝ68፥25፤ከኤር31፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥5፤ *ገዥዎቿ፤* በዘዳ28፥44 መሠረት ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "የበላዮቿ" ማለት ነው (ከዘዳ28፥13 ጋር ያነጻጽሩ)። *ተመችቶአቸዋል፤* ኤር12፥1 ይመ።

1፥6፤ *የጽዮን ሴት ልጅ፤* ኢየሩሳሌምና ነዋሪዎቿ በሰውኛ ዘይቤ ተገልጸዋል። *መሳፍንቶቿ ... በአሳዳጆቻቸው ፊት ... ሸሹ፤* ኤር 52፥7-8 ይመ።

*1፥7 በተጨነቀችባቸውና በተንከራተተችባቸው፤* 3፥19 ይመ። *ሀብት፤* ቍ10-11 ይመ። *በጥንት ዘመን፤* ለምሳሌ እንደ ዳዊትና እንደ ሰሎሞን ዘመነ መንግሥት ዐይነት ማለት ነው። *በጠላት እጅ በወደቁ ጊዜ፤* 2ሳሙ24፥14 ይመ። *በመፈራረሷም፤* በቁሙ፣ 'ማቆም' ማለት ነው። በዕብራይስጥ የዚህ ቃልና የ 'ሰንበት' ሥርወ ቃል ተመሳሳይ ነው። ምናልባት ምፀታዊ የቃላት ጨዋታ ሳይሆን አይቀርም።

1፥8 *የረከሰች፤* ቍ17 እና ማብ ይመ። የወር አበባዋ በሚመጣበት ጊዜ በሥርዐታቸው መሠረት ርኩስ የምትሆነውን ሴት ያመለክታል (ዘሌ12፥2፡5፤15፥19 ይመ)፤ እዚህ ላይ ኢየሩሳሌም በሰውኛ ዘይቤ በሴት ተመስላለች (ቍ6 ይመ)።

1፥9 *ርኵሰቷ፤* ሆን ተብሎ በተሠራ ኀጢአት ምክንያት፣ እንደ ሥርዐታቸው ልማድ መርከስን ያሳያል (የዘሌ4፥12 ማብ ይመ)። *ወደ ፊት የሚሆንባትን አላሰበችም፤* ኢሳ47፥7 ይመ። *እግዚአብሔር ሆይ፤ ... ተመልከት፤* ቍ11 እና 20 ይመ። *ጠላት ድል አድርጎአልና፤* ቍ16 ይመ።

1፥10 *ወደ ጉባኤህ እንዳይገቡ የከለከልሀቸው፤* ሕዝ44፥7

ጣዖት የሚያመልኩ አሕዛብ፣
ወደ መቅደሷ ሲገቡ አየች::

11ካፍ እንጀራ በመፈለግ፣
ሕዝቧ ሁሉ በሥቃይ ይጮኻል፤
በሕይወት ለመኖር፣
የከበረ ሀብታቸውን በምግብ ይለውጣሉ፤
"አቤቱ እግዚአብሔር ሆይ፤ አስበኝ፤
ተመልከተኝም፤
እኔ ተዋርጃለሁና"

12ላሜድ "እናንተ መንገድ ዐላፊዎች
ሁሉ፤ ይህ ለእናንተ ምንም
አይደለምን?
ተመልከቱ፤ እዩም፤
በጽኑ ቍጣው ቀን፣
እግዚአብሔር ያመጣብኝን፣
በእኔ ላይ የደረሰውን፣
የእኔን መከራ የመሰለ መከራ አለን?

13ሜም "ከከፍታ ስፍራ እሳትን ላከ፤
ወደታች ወደ ዐጥንቶቼም ሰደደው፤
በእግሮቼ ላይ መረብ ዘረጋ፤
ወደ ኋላም ጣለኝ፤
ቀኑን ሙሉ በማድከም፣
ባዶ አድርጎ አስቀመጠኝ::

14ኖን "ኀጢአቶቼ ቀንበር ሆኑ፤[^]
በእጆቹ አንድ ላይ ተገመዱ፤
በዐንገቴም ላይ ተጭነዋል፤
ኀይሌንም አዳከመ፤
ልቋቋማቸው ለማልችላቸው፣
እርሱ አሳልፎ ሰጠኝ::

15ሳምኬት "በውስጤ ያሉትን ተዋጊዎች ሁሉ፣
እግዚአብሐር ተቃወመ፤
ጕልማሶቼን ለማድቀቅ፣
ሰራዊት በላዬ ላይ ጠራ[*]፤
ድንግሊቱን የይሁዳ ሴት ልጅ፣
እግዚአብሐር በወይን መጭመቂያ ውስጥ
ረገጣት::

16"የማለቅሰው ስለ እነዚህ ነገሮች ነው፤
ዐይኖቼ በእንባ ተሞልተዋል፣
ሊያጽናናኝ የቀረበ፣
መንፈሴንም ሊያረጋጋ የሞከረ ማንም
የለም፤
ጠላት በርትቶአልና
ልጆቼ ተጨንቀዋል::"

17ፌ ጽዮን እጆቿን ዘረጋች፤
የሚያጽናናትም የለም፤
ጎረቤቶቹ ጠላቶቹ እንዲሆኑ፣
እግዚአብሔር በያዕቆብ ላይ ትእዛዝ
አውጥቶአል፤
ኢየሩሳሌምም በመካከላቸው፣
እንደ ርኩስ ነገር ተቈጠረች::

18ጻዴ "እግዚአብሔር ጻድቅ ነው፤
እኔ ግን በትእዛዙ ላይ ዐመፅ አድርጌ
ነበር፤
እናንተ ሕዝቦች ሁሉ ስሙ፤
መከራዬንም ተመልከቱ፤
ወይዛዝርቶቼና ጕበዛዝቶቼ፣
ተማርከው ሄደዋል::

19ቆፍ "ወዳጆቼን ጠራኋቸው፤
እነርሱ ግን ከዱኝ፤
ካህናቶቼና ሽማግሌዎቼ፣
ሕይወታቸውን ለማትረፍ፣
ምግብ ሲፈልጉ፣
በከተማዪቱ ውስጥ አለቁ::

20ሬስ "አቤቱ እግዚአብሔር ሆይ፤ እንዴት
ተጨንቄአለሁ!
በውስጤ ተሠቃይቼአለሁ፤
በልቤ ታውኬአለሁ፤
እጅግ ዐመፀኛ ሆኛለሁና፤
በውጭ ሰይፍ ይፈጃል፤
በቤትም ውስጥ ሞት አለ::

21ሳን "ሰዎች የሥቃይ ልቅሶዬን ሰሙ፤
የሚያጽናናኝ ግን ማንም የለም፤
ጠላቶቼ ሁሉ ጭንቀቴን ሰሙ፤
አንተ ባደረግኸውም ደስ አላቸው፤
አቤቱ የተናገርኸት ቀን ትምጣ፤
እነርሱም እንደ እኔ ይሁኑ::

1÷11 መዝ6÷6፤ 38÷8፤ኤር37÷21፤52÷6
1÷12 ቊ18፤ኢሳ 10÷4፤13÷13፤ኤር 18÷16፤30÷24
1÷13 ኢዮ18÷8፤ 30÷30፤መዝ102÷3፤ ኤር44÷6፤ዕን3÷16
1÷14 ዘዳ28÷48፤ ኢሳ 47÷6፤ኤር 15÷12፤32÷5
1÷15 መሳ6÷11፤ኢ ሳ5÷5፤28÷18፤41÷2፤ ኤር14÷17፤18÷21፤3 7÷10
1÷16 ቊ2፤ኢዮ 7÷3፤መዝ69÷20፤119 ÷136፤መክ4÷1፤ኢሳ 22÷4፤ኤር13÷17፤ 14÷17፤16÷7፤ ሰቆ 2÷11:18፤3÷48-49
1÷17 ዘፀ23÷21፤ዘሌ 18÷25-28፤ኤር2÷22፤ 4÷31
1÷18 ቊ12፤ዘፀ9÷27፤ ዘዳ28÷32:41፤1ሳሙ 12÷14፤ዕዝ9÷15
1÷19 ኤር14÷15፤ 22÷20፤ሰቆ2÷20
1÷20 ቊ8፤ዘዳ 32÷25፤ ኤር4÷19፤ሰቆ2÷11፤ ሕዝ7÷15
1÷21 ቊ4:8፤ መዝ 6÷6፤38÷8፤ኢሳ47÷11፤ ኤር30÷16፤ሰቆ2÷15

^14 አብዛኛዎቹ የዕብራይስጥ ቅጆች እንዲሁ ሲሆኑ ሰብዓ ሊቃናት ግን ኀጢአቶቼን ያለማጸረተ ይከታተላል ይላል::
*15 ወይም ...በሚያደቅበት ጊዜ፣ ለኔ ጊዜን ወሰነልኝ::

እና 9 ይመ::

1÷11 *እንጀራ በመፈለግ፤* ኢየሩሳሌም በተከከበች ጊዜና ከዚያም በኋላ ዘወትር የምግብ እጥረት ነበር:: *በሕይወት ለመኖር፤* ቊ19፤1ሳሙ30÷12 ይመ::

*1÷12፤* ቊ18 ይመ:: እስከዚህ ድረስ ዋና ተናጋሪው ጸሐፊው ራሱ ነበር፤ ከምዕራፍ አንድ አጋማሽ በኋላ ግን፣ ዋና ተናጋሪው በሰውኛ ዘይቤ የተገለጠችው ኢየሩሳሌም ሆና እናገኛታለን:: *በጽኑ ቍጣው፤* 2÷3:6፤4÷11 ይመ:: ይህ ዐይነቱ አገላለጽ በትንቢተ ኤርምያስ የተለመደ ነው (ኤር4÷8:26፤12÷13፤25÷37-38፤44÷6፤ 49÷37፤ 51÷45 ይመ)::

1÷13 *ከከፍታ ስፍራ እሳትን ላከ፤* 1ነገ18÷38፤ 2ነገ1÷10: 12:14፤2ዜና7÷1፤ ይመ:: *ዐጥንቶቼም፤* በሰዉኛ ዘይቤ በሴት የተመሰለችው፣ የኢየሩሳሌም ዐጥንት ማለት ነው (የቊ8 ማብ ይመ):: እጅግ በሚመሳሰል ሁኔታዎች የእግዚአብሔር ቃል በነ ቢዩ ዐጥንት ውስጥ እንደሚነድድ እሳት ሆኖ ነበር (ኤር 20÷9 እና ማብ ይመ):: *በእግሮቼ ላይ መረብ ዘረጋ፤* መዝ57÷6፤ ምሳ29÷5 ይመ:: *ባዶ፤* እንደ አቤሴሎም እኅት ትዕማር ማለት ነው (2ሳሙ13÷20 ይመ)::

1÷15 *በወይን መጭመቂያ ውስጥ ረገጣት፤* መለኮታዊን ፍርድ የሚያመለክት የተለመደ ዘይቤያዊ አገላለጽ ነው (ኢሳ63÷2-3፤ኢዮ 3÷13፤ራእ14÷19-20፤19÷15 ይመ):: *ድንግሊቱን የይሁዳ ሴት ልጅ፤* 2÷13 እንዲሁም የ2ነገ19÷21፤የኤር14÷17 ማብ ይመ::

1÷16 *ዐይኖቼ በእንባ ተሞልተዋል፤* (3÷48፤ኤር9÷18፤ 13÷17፤ 14÷17፤እንዲሁም ኤር9÷1 ይመ):: *ጠላት በርትቶአልና፤* ቊ9 ይመ::

1÷17 *ጠላቶቹ እንዲሆኑ፤* ቊ2 ይመ:: *ርኩስ ነገር፤* የቊ8 ማብ ይመ በሌላ ቦታ ያለውን ተመሳሳይ ምስል በዕዝ9÷11፤ በኢሳ 30÷22፤64÷6፤በሕዝ7÷19-20 ይመ::

1÷18 *እግዚአብሔር ጻድቅ ነው፤* ዘዳ32÷4፤2ዜና12÷6፤ መዝ 119÷137፤ኤር12÷1፤ እንዲሁም የመዝ4÷1 ማብ ይመ:: *በትእዛዙ ላይ ዐመፅ አድርጌ ነበር፤* ዘኊ20÷24 ይመ:: *እናንተ ሕዝቦች ሁሉ ስሙ፤* 1ነገ22÷28፤ መዝ49÷1፤ ሚክ1÷2 ይመ::

1÷19 *ወዳጆቼ ... ከዱኝ፤* ቍ2እና ማብ ይመ:: *ሕይወታቸውን ለማትረፍ፤* የቍ11 ማብ ይመ::

1÷20 *በውስጤ ተሠቃይቼአለሁ፤* በ2÷11 ላይ ተደግሞአል:: *በውስጤ...በውጭ፤* ኤር14÷18 ይመ::

1÷21 *የተናገርኸት ቀን፤* እግዚአብሔር በአሕዛብ ላይ የሚፈርድ በት ቀን ማለት ነው (ኤር25÷15-38 ይመ)::

22ታው፤ "ክፋታቸው ሁሉ በፊትህ ይቅረብ፤
ከኀጢአቴ ሁሉ የተነሣ፣
በእኔ ላይ እንዳደረግኸብኝ፣
በእነርሱም ላይ አድርግባቸው፤
የሥቃይ ልቅሶዬ በዝቶአል፤
ልቤም ደክሞአል።"

# 2

አሌፍ፤– እግዚአብሔር የጽዮንን ሴት ልጅ፣
በቍጣው ደመና እንዴት ጋረዳት!ʷ
ከሰማይ ወደ ምድር፣
የእስራኤልን ክብር ወርውሮ ጣለው፤
በቍጣው ቀን፣
የእግሩን መቀመጫ አላስታወሰም።

2ቤት፤ የያዕቆብን መኖሪያ ሁሉ፣
እግዚአብሔር ያለ ርኅራኄ ዋጣቸው፤
የይሁዳን ሴት ልጅ ምሽጎች፣
በቍጣው አፈረሳቸው፤
መንግሥቷንና መሳፍንቷን፣
በማዋረድ ወደ ምድር ጣላቸው።

3ጋሜል፤ በጽኑ ቍጣው፣
የእስራኤልን ቀንድ ሁሉሶ ሰበረ፤
ጠላት በተቃረበ ጊዜ፣
ቀኝ እጁን ወደ ኋላ መለሰ፤
በዙሪያው ያለውን ሁሉ እንደሚበላ እሳት፣
በያዕቆብ ላይ የእሳት ነበልባል ነደደ።

4ዳሌጥ፤ እንደ ጠላት ቀስቱን ገተረ፤
ቀኝ እጁ ተዘጋጅታለች፤
ለዐይን ደስ የሚያሰኙትን ሁሉ፤
እንደ ጠላት ዐረዳቸው፤
በጽዮን ሴት ልጅ ድንኳን ላይ፣
ቍጣውን እንደ እሳት አፈሰሰ።

5ሄ፤ እግዚአብሔር እንደ ጠላት ሆነ፤
እስራኤልንም ዋጠ፤
ቤተ መንግሥቶቿን ሁሉ ዋጠ፤
ምሽጎቿን አፈራረሰ፤
በይሁዳ ሴት ልጅ፣
ለቅሶንና ሰቈቃን አበዛ።

6ዋው፤ ማደሪያውን እንደ አትክልት ስፍራ
ባዶ አደረገ፤
መሰብሰቢያ ስፍራውን አፈረሰ፤
እግዚአብሔር ጽዮንን፣
ዓመት በዓላቶቿንና ሰንበታቷን
እንድትረሳ አደረጋት፤
በጽኑ ቍጣው፣
ንጉሡንና ካህኑን እጅግ ናቀ።

7ዛይ፤ እግዚአብሔር መሠዊያውን ናቀ፤
መቅደሱንም ተወ፤
የቤተ መንግሥቶቿን ቅጥሮች፣
ለጠላት አሳልፎ ሰጠ፤
በዓመት በዓል ቀን እንደሚደረገው
በእግዚአብሔር ቤት በኀይል ጮኹ።

8ሔት፤ በጽዮን ሴት ልጅ ዙሪያ ያለውን ቅጥር፣
እግዚአብሔር ለማፍረስ ወሰነ፤
የመለኪያ ገመድ ዘረጋ፤
ከማጥፋትም እጆቹን አልሰበሰበም፤
ምሽጎችና ቅጥሮች እንዲያለቅሱ አደረገ፤
በአንድነትም ጠፉ።

9ጤት፤ በሮቿ ወደ ምድር ሰመጡ፤
የብረት መወርወሪያዎቻቸውን ሰባበረ፤
አጠፋቸውም፤
ንጉሥዋና መሳፍንቶቿ በአሕዛብ መካከል
ተማርከው ተሰደዋል፤
ሕጉ ከእንግዲህ አይኖርም፤
ነቢያቶቿም ከእንግዲህ፣
ከእግዚአብሔር ራእይ አያገኙም።

10ዮድ፤ የጽዮን ሴት ልጅ ሽማግሌዎች፣
በምድር ላይ በዝምታ ተቀምጠዋል፤
በራሳቸው ላይ ትቢያ ነሰነሱ፤
ማቅም ለበሱ፤
የኢየሩሳሌም ወጣት ሴቶች፣
ራሳቸውን ወደ ምድር ዝቅ አደረጉ።

1፥22 ቍ8፤ነህ4፥5፤መዝ6፥6
2፥1 መዝ99፥5፤ 132፥7፤ኤር12፥7፤ሰቆ3፥44
2፥2 ቍ17፤መዝ 21፥9፤89፥39-40፤ኢሳ 25፥12፤ሰቆ3፥43
2፥3 መዝ74፥11፤ 75፥5፡10፤ኢሳ42፥25፤ ኤር21፥4-5፡14
2፥4 2ዜና34፥21፤ኢዮ 3፥23፤16፥13፤መዝ48 ፥2፤ኢሳ 42፥25፤ኤር 4፥20፤7፥20፤ሰቆ3፥ 12-13፤ሕዝ20፥34፤ 24፥16፡25
2፥5 ቍ2፤ኢዮ13፥ 24፤ኢሳ29፥2፤ኤር7፥ 20፤9፥17-20
2፥6 2ዜና36፥19፤ኢሳ 43፥28፤ኤር7፥14፤52 ፥13፤ሰቆ4፥16፤5፥12፤ ሶፎ3፥18
2፥7 ዘሌ26፥31፤ መዝ 74፥7-8፤ኢሳ 64፥11፤ኤር21፥4፤ 33፥4-5፤52፥13፤ሕዝ 7፥21-22፡24
2፥9 ዘዳ28፥36፤ 1ሳሙ 3፥1፤2ነገ24፥15፤2ዜና 15፥3፤ነህ1፥3፤ኢሳ 45፥2፤ኤር14፥14፤ 16፥13፤ሆሴ3፥4፤11፥6
2፥10 ኢሱ7፥6፤ኢዮ 2፥12፡13፤ኢሳ3፥24፡ 26፤ሰቆ3፥28፤ሕዝ27፥ 30-31

*-1 ይህ ምዕራፍ ጥቅሶቹ ተከታታይ ፊደላት ባሉት የዕብራይስጥ ሆሄያት የሚጀምር፣ የመጀመሪያው ወይም የመጨረሻው መስመር ትርጕም የሚሰጥ ቃል ወይም ዐረፍተ ነገር ያለው ግጥም ነው።*
*-1 ወይም እግዚአብሔር በቍጣው የጽዮንን ሴት ልጅ እንዴት አዋረዳት!*
*ሶ3 ወይም ብርታትን ሁሉ፤ ወይም ንጉሥ ሁሉ፤ ቀንድ በዚህ ቦታ ብርታትን ያመለክታል።*

1፥22 *ክፋታቸው ... በፊትህ፤* መዝ109፥14-15 ይመ። *ልቤም ደክሞአል፤* ይኸው ዐይነት አገላለጽ በኤር 8፥18 ይገኛል፤ ሰቆ 5፥17፤ ኢሳ1፥5 ይመ።

2፥1 *የጽዮንን ሴት ልጅ፤* 1፥6 እና ማብ ይመ። *"እንዴት ...!"* የ1፥1 ማብ ይመ። *የእስራኤልን ክብር ወርውሮ ጣለው፤* ምስያው ተምዘግዝጎ እንደሚወድቅ ኮከብ ዐይነት ነው (ይኸውም በኢሳ 14፥12 ላይ እንዳለው ማለት ነው)። *የእግሩን መቀመጫ፤* ይህም 1) የቃል ኪዳኑ ታቦት (1ዜና28፥2 ይመ) ወይም ምናልባት 2)የጽዮን ተራራ ሊሆን ይችላል (መዝ99፥5፡9 ይመ)።

2፥2 *መኖሪያ ሁሉ...ዋጣቸው፤* ቍ5 ይመ። *የይሁዳን ሴት ልጅ፤* የ1፥15 ማብ ይመ።

2፥3 *ቀንድ ሁሉ ሰበረ፤* ኤር48፥25 ይመ። *እንደሚበላ... የእሳት ነበልባል፤* ዘኍ11፥3፤ኢዮ1፥16፤መዝ106፥18 ይመ።

2፥4 *ቀስቱን ገተረ፤* ዘዳ32፥42፤ መዝ7፥12-13፤ዘካ9፥13-14 ይመ። *ቍጣውን ... አፈሰሰ፤* መዝ 69፥24፤ 79፥6፤ ኤር 6፥11፤ 7፥20፤ 10፥25፤ 42፥18፤ 44፥6፤ ሆሴ5፥10፤ ሶፎ3፥8 ይመ።

2፥5 *ቤተ መንግሥቶቿን...ምሽጎቿን፤* ሆሴ8፥14 ይመ። *በይሁዳ ሴት ልጅ፤* የ1፥15 ማብ ይመ።

2፥6 *ማደሪያውን፤* በመጀመሪያ ማደሪያ ድንኳኑን፣ ከጊዜ በኋላ ደግሞ ቤተ መቅደሱን ይመለከታል (መዝ27፥4-5 ይመ)። *እንደ አትክልት ስፍራ፤* ከኢሳ5፥5-6፤ከኤር5፥10፤12፥10 ጋር ያነጻጽሩ። *መሰብሰቢያ ስፍራውን፤* እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የሚገናኝበት ማደሪያ ድንኳን ወይም ቤተ መቅደስ ማለት ነው (ዘፀ25፥22፤ 29፥42-43፤ መዝ74፥4 ይመ)።

2፥7 *ናቀ ... ተወ፤* እነዚህ ሁለት ግሶች ጌታ ንጉሡን ከዳዊት ሥርወ መንግሥት መሠረዙን ከሚናገረው መዝ89፥38-39 ውስጥ፣ "ናቅኸው፤ ጣልኸውም" በሚል ይገኛሉ። *በዓመት በዓል ቀን እንደሚደረገው፤* ሆሴ12፥9 ይመ። *በእግዚአብሔር ቤት በኀይል ጮኹ፤* መዝ74፥4 ይመ።

2፥8 *በጽዮን ሴት ልጅ፤* ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን በሰውኛ ዘይቤ የሚገልጽ ነው። *ለማፍረስ ወሰነ፤* ኤር32፥31 ይመ። *የመለኪያ ገመድ ዘረጋ፤* በተመሳሳይ ትክክለኛ ሚዛንና ለግንቡ ሥራ በዋለው ጥሬ ዕቃዎች ለማጥፋት ሲባል ነው (ኢሳ28፥17 እና ማብ፤ አሞ7፥7-8 እና ማብ ይመ)። *ምሽጎችና ቅጥሮች፤* ኢሳ 26፥1 ይመ። ምሽጎቹ የውጭ ቅጥሮች ነበሩ (2ሳሙ20፥15 ይመ)።

2፥9 *ነቢያቶቿም ከእንግዲህ ... ራእይ አያገኙም፤* ጌታ በነቢያቱ በኩል ሕዝቡን አይናገራቸውም ነበር (መዝ74፥9፤ አሞ 8፥11 እና ማብ፤ ሚክ3፥7 ይመ)።

2፥10 *ሽማግሌዎች፤* የዘፀ3፥16 ማብ ይመ። *በምድር ላይ በዝምታ ተቀምጠዋል፤ በራሳቸው ላይ ትቢያ ነሰነሱ፤ ማቅም ለበሱ ... ራሳቸውን ወደ ምድር ዝቅ አደረጉ፤* እነዚህ ሁሉ የሐዘን መግለጫ ምልክቶች ናቸው (ኢዮ2፥12-13፤መዝ35፥13-14)።

11ካፍ፤ ዐይኔ በለቅሶ ደከመ፤
  ነፍሴ በውስጤ ተሠቃየች፤
ልቤም በሐዘን ፈሰሰች፣
  በከተማዪቱ መንገዶች ላይ፣
ሕዝቤ ተደምስሰዋልና፤
  ልጆችና ሕፃናት ደክመዋልና።

12ላሜድ፤ በከተማዪቱ መንገዶች ላይ፣
  እንደ ቈሰሉ ሰዎች ሲደክሙ፣
በእናታቸው ክንድ ላይ፣
  ነፍሳቸው በመውጣት ላይ ሳለች፣
"እንጀራና የወይን ጠጅ የት አለ?"
  እያሉ እናቶቻቸውን ይጠይቃሉ።

13የኢየሩሳሌም ሴት ልጅ ሆይ፤ ስላንቺ
    ምን ማለት እችላለሁ?
ከምንስ ጋር አወዳድርሻለሁ? ድንግሊቱ
    የጽዮን ልጅ ሆይ፤
አጽናናሽ ዘንድ፣
  በምን ልመስልሽ እችላለሁ?
ቍስልሽ እንደ ባሕር ጥልቅ ነው፤
  ማንስ ሊፈውስሽ ይችላል?

14ኖን፤ የነቢያቶችሽ ራእይ፣
  ሐሰትና ከንቱ ነው፤
ምርኮኛነትሽን ለማስቀረት፣
  ኀጢአትሽን አይገልጡም።
የሚሰጡሽም የትንቢት ቃል፣
  የሚያሳስትና ከመንገድ የሚያወጣ ነው።

15ሳምኬት፤ በአጠገብሽ የሚያልፉ ሁሉ፣
  እጃቸውን ያጨበጭቡብሻል፤
"የውበት መደምደሚያ፣ የምድር ሁሉ
    ደስታ፣
የተባለች ከተማ ይህች ናትን?"
  እያሉ ራሳቸውን በመነቅነቅ፣
በኢየሩሳሌም ሴት ልጅ ላይ ያሾፋሉ።

16ዔ፤ ጠላቶችሽ ሁሉ በአንድ ላይ፣
  አፋቸውን በኀይል ከፈቱ፤
ጥርሳቸውን እያፏጩ ያሾፋሉ፤
  እንዲህም አሉ፤ "ውጠናታል፤
የናፈቅነው ጊዜ ይህ ነበር፤
  ኖረንም ልናየው በቃን።"

17ፌ፤ እግዚአብሔር ያሰበውን አደረገ፤
  ከረዥም ጊዜ በፊት የተናገረውን፣
ቃሉን ፈጸመ፤
  ያለ ርኅራኄ አፈረሰሽ፤
ጠላት በሥቃይሽ ላይ እንዲደሰት፣
  የጠላትሽንም ቀንድ[a] ከፍ ከፍ አደረገ።

18ጻዴ፤ የሕዝቡ ልብ፣ ወደ እግዚአብሔር
    ጮኸ።
የጽዮን ሴት ልጅ ቅጥር ሆይ፤
  ቀንና ሌሊት፣
እንባሽ እንደ ወንዝ ይፍሰስ፤
  ለራስሽ ዕረፍትን አትስጪ፣
ዐይኖችሽ ከማንባት አያቋርጡ።

19ቆፍ፤ የሌሊቱ ሰዓት ሲጀምር፣
  ተነሺ በሌሊት ጩኺ፤
በእግዚአብሔር ፊት፣
  ልብሽን እንደ ውሃ አፍስሺ፤
በየመንገዱ ዳር ላይ፣ በረሀብ ስለወደቁት፣
  ስለ ልጆችሽ ሕይወት፣ እጆችሽን ወደ
    እርሱ አንሺ።

20ሬስ፤ አቤቱ እግዚአብሔር ሆይ እይ፤
      ተመልከትም፤
  በማን ላይ እንዲህ አድርገህ ታውቃለህ?
በውኑ እናቶች ሕፃኖቻቸውን፣
  ተንከባክበው ያሳደጓቸውን ልጆች
    ይብሉን?
ካህኑና ነቢዩስ፣
  በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ውስጥ
    ይገደሉን?

21ሳን፤ በየመንገዱ ዐቧራ ላይ፣

[a] 17 ቀንድ በዚህ ቦታ ብርታትን ያመለክታል

2፥11 ቍ19፤ኢዮ 30፥27፤መዝ22፥14፤119፥82፤ኢሳ1፥5፤15፥3፤ኤር9፥1፤ሰቆ1፥16፤1፥20፤3፥48-51፤4፥4
2፥12 ኢዮ3፥24፤ኢሳ 24፥11፤ሰቆ4፥4
2፥13 2ነገ19፥21፤ኢሳ 1፥6፤37፥22፤ኤር14፥17፤30፥12-15፤ሰቆ 1፥12
2፥14 ኤር2፥8፤ 8፥11፤20፥6፤23፥25-32፤33-40፤28፥15፤29፥9፤ሕዝ 13፥3፤22፥28
2፥15 ዘኍ24፥10፤ ዘዳ 28፥37፤ኢዮ16፥4፤መዝ45፥11፤48፥2፤50፥2፤ኢሳ28፥22፤ ኤር19፥8፤ሰቆ1፥21፤ ሕዝ16፥14፤25፥6፤ ናሆ3፥19
2፥16 ኢዮ16፥9፤ መዝ 22፥13፤35፥25፤ ሰቆ3፥46፤ሕዝ36፥3፤ ሚክ4፥11
2፥17 ቍ2፤ዘዳ 28፥15-45፤ መዝ 22፥17፤ 89፥42፤ኢሳ 44፥26፤ኤር39፥16፤ሰቆ 1፥5፤ ሕዝ5፥11፤7፥9፤8፥18፤ዘካ1፥6
2፥18 ቍ8፤መዝ 119፥145፤ኤር9፥1፤ ሰቆ1፥16፤3፥49
2፥19 ቍ11፤1ሳሙ 1፥15፤መዝ28፥2፤ኢሳ 26፥9፤51፥20
2፥20 ዘዳ28፥53፤ መዝ78፥64፤ኤር14፥15፤23፥11-12፤19፥9፤ ሰቆ1፥19፤4፥10፤ሕዝ 5፥10
2፥21 ዘዳ32፥25፤ 2ዜና36፥17፤መዝ78፥62-63፤ኤር6፥11፤13፥14፤ሰቆ3፥43፤ዘካ11፥6

*የኢየሩሳሌም ወጣት ሴቶች፤* 1፥4 እና ማብ ይመ።

2፥11 *ዐይኔ ... ደከመ፤* የመዝ6፥7 ማብ ይመ። *በለቅሶ፤* የ1፥16 ማብ ይመ። *በውስጤ ተሠቃየች፤* የተደገመ ሐረግ ነው (1፥20 ይመ)። *ሕዝቤ፤* በቀጥታ "የወገኔ ሴት ልጅ" ማለት ነው (3፥48፤4፥10፤ እንዲሁም የኤር14፥17 ማብ ይመ)።

2፥12 *ነፍሳቸው በመውጣት ላይ ሳለች፤* ኢዮ 30፥16፤ መዝ107፥5፤ ዮና2፥7 ይመ።

2፥13 *የኢየሩሳሌም ሴት ልጅ ... ድንግሊቱ የጽዮን ልጅ ሆይ፤* የ1፥6 ማብ፤ ኤር14፥17 ይመ። *ስላንቺ ምን ማለት እችላለሁ?፤* ኢዮ 29፥11 ይመ።

2፥14 *የነቢያቶችሽ ... ሐሰትና፤* ኤርምያስ ብዙ ጊዜ ሐሰተኛ ነቢያትን ያወግዛል (ኤር5፥12-13፤6፥13-15፤8፥10-12፤14፥13-15፤ 23፥9-40፤ 27፥9-28፥17 ይመ)። *ከንቱ፤* ወይም የታይታ ሰዎች ማለት ነው፤ ይህ ምስያ እንዴት እንደተብራራ ለማስተዋል፤ ሕዝ 13፥10-16፤22፥28 ይመ። *ከመንገድ የሚያወጣ፤* ይህን ቃል በአ ጽንዖት የሚገልጸው ያልተለመደው የዕብራይስጥ ቃል በኤር 27፥10፡15 ላይ፣ "እንድትጠፉ" በሚል በአጽንዖት ከተገለጸው ጋር ተመሳሳይ የሆነ ሥረወ ቃል አለው። የሐሰተኛ ነቢያት ቅጥ ፊት ሰዎችን ያስታል፤ ጌታ እንዲፈርድባቸውም ያደርጋሉ። ሐሰ ተኛ ነቢያቱም ባመጡት መዘዝ የተነሣ ጥፋት ይደርስባቸዋል።

2፥15 *በአጠገብሽ የሚያልፉ ሁሉ፤* 1፥12 ይመ። *እጃቸውን ያጨበጭቡብሻል፤* ኢዮ27፥23 ይመ። *ያሾፋሉ፤* ቍ16 ይመ፤ እን ዲሁም የኤር19፥8 ማብ ይመ። *የውበት መደምደሚያ፤* በመዝ50፥2 ላይ እንደተመለከተው ነው፤ ማብ ይመ። *የምድር ሁሉ ደስታ፣ የተባለች፤* በመዝ 48፥2 ላይ እንደ ተመለከተው ማለት ነው፤ የዚህኑ ማብ ይመ፤ ከኤር 51፥41 ጋር ያነጻጽሩ)። *ራሳቸውን በመነቅነቅ፤* የኢዮ 16፥4 ማብ ይመ። እንዲሁም መዝ44፥14፤109፥25፤ ኤር 18፥16 ይመ። *በኢየሩሳሌም ሴት ልጅ፤* የ1፥6፤ የኤር14፥17 ማብ ይመ።

2፥16 *ውጠናታል፤* ቍ2፡5፤ ኤር51፥34 ይመ።

2፥17 *ከረዥም ጊዜ በፊት፤* በሙሴ ዘመን ማለት ነው (ለምሳ ሌም በዘሌ26፥23-39፤ በዘዳ 28፥15-68 ላይ የሰፈረውን አስፈሪ መዓት ይመ)። *ቃሉን ፈጸመ፤* ኢሳ55፥11 እና ማብ ይመ። *ቀንድ ከፍ ከፍ አደረገ፤* ኀይሉን አበረታ፤ (አማራጭ ትርጕሙን እንዲሁም 1ሳሙ2፥1፤ መዝ75፥4 ይመ)።

2፥18 *እንባሽ ... ይፍሰስ፤* እግዚአብሔር የተረፉትን ሕዝቦች የምልጃ ጩኸት እንደሚሰማ ተስፋ በማድረግ፣ ኤርምያስ ሕዝቡ እንዲጸልዩ፤ እንዲያለቅሱና ንስሓ እንዲገቡ ጥሪ ያቀርባል (ከቍ19 ጋር ያነጻጽሩ) ኤር14፥17 ይመ። *ቅጥር ሆይ፤* በኢሳ 14፥31 ላይ የከተማዋ ቅጥር በተመሳሳይ መልክ ተጠርታለች። *የጽዮን ሴት ልጅ ... ሆይ፤* ኢየሩሳሌምንና ኗሪዎቿን በሰውኛ ዘይቤ የሚገ ልጽ ነው።

2፥19 *የሌሊቱ ሰዓት ሲጀምር፤* የመሳ7፥19 ማብ እንዲሁም መዝ63፥6 ይመ። *ልብሽን ... አፍስሺ፤* ከልብ በሆነ ጸሎት ማለት ነው (መዝ62፥8 ይመ)። *እንደ ውሃ፤* "አፍስስ" ወይም "አፍስሺ" ከሚለው ጋር የተለመደ ተነጻጻሪ ዘይቤ ነው (ዘዳ12፥16፡24፤ 15፥23፤ መዝ 79፥3፤ ሆሴ5፥10 ይመ)። *እጆችሽን ... አንሺ፤* በጸሎትና በምስጋና ማለት ነው (መዝ28፥2፤63፥4፤1ጢሞ 2፥8 ይመ)። *በረሀብ ስለወደቁት ... ልጆችሽ፤* ቍ11-12ይመ።

*2፥20-22፤* በቍ19 ላይ ጸሎት ይደረግ ዘንድ የቀረበ ጥሪ ነው።

2፥20 *እናቶች ሕፃኖቻቸውን ... ይብሉን?* የኤር19፥9 ማብ ይመ።

*2፥21፤* ኤር6፥11 እና ማብ ይመ።

ወጣትና ሽማግሌ በአንድነት ወደቁ፤
ወይዛዝርቴና ጕበዛዝቴ፣
በሰይፍ ተገደሉ፤
በቍጣህ ቀን ገደልሃቸው፤
ያለ ርኅራኄም ዐረድሃቸው።

22ታው፤ "በበዓል ቀን ለግብዣ እንደምትጠራ፣
ሽብርን ከየአቅጣጫው በእኔ ላይ ጠራህ፤
*በእግዚአብሔር የቍጣ ቀን*፣
ማንም አላመለጠም ወይም አልተረፈም፤
የተንከባከብኋቸውንና ያሳደግኋቸውን፣
ጠላቴ አጠፋብኝ።"

3 አሌፍ[*1] በቍጣው በትር፣
መከራ ያየ ሰው እኔ ነኝ።
2ከፊቱ አስወጣኝ፤
በብርሃን ሳይሆን በጨለማ እንድሄድ
አደረገኝ።
3በእርግጥ ቀኑን ሁሉ በመደጋገም፣
እጁን በላዬ ላይ መለሰ።

4ቤት፤ እርሱ ሥጋዬንና ቈዳዬን አስረጀ፤
ዐጥንቶቼንም ሰባበረ።
5በምሬትና በድካም፣
ቅጥር ሠራብኝ፤ ዙሪያዬንም ከበበኝ።
6ከሞቱ ብዙ ጊዜ እንደሆናቸው፣
በጨለማ እንድኖር አደረገኝ።

7ጋሜል፤ በቅጥር ውስጥ ዘጋብኝ፤ ስለዚህ
ማምለጥ አልቻልሁም፤
የእስር ሰንሰለቴንም አከበደብኝ።
8ርዳታ ፈልጌ ብጣራና ብጮኽ እንኳ፣
ጸሎቴን መስማት አልፈለገም።
9መንገዴን በተጠረቡ ድንጋዮች ዘጋ፤
ጐዳናዬንም አጣመመ።

10ዳሌጥ፤ አሸምቆ እንደ ተኛ ድብ፣
እንደ አደባም አንበሳ፣
11ከመንገድ ጐትቶ አስወጣኝ፤ ቈራረጠኝም፤
ያለ ረዳትም ተወኝ።
12ቀስቱን ገተረ፤
ለፍላጻዎቹም ዒላማ አደረገኝ።

13ሄ፤ ፍላጻዎችን ከሰገባው አውጥቶ፣
ልቤን ወጋው።
14ለሕዝቤ ሁሉ ማላገጫ ሆንሁኝ፤
ቀኑን ሙሉ በመሣለቅ ያዜሙብኛል።
15መራራ ሥር አበላኝ፤
ሐሞትም አጠገበኝ።

16ዋው፤ ጥርሴን በድንጋይ ሰበረ፤
በትቢያ ውስጥ ረጋገጠኝ።
17ነፍሴ ሰላምን አጣች፤
ደስታ ምን እንደ ሆነ ረሳሁ።
18ስለዚህ፣ "ክብሬ፣
ከእግዚአብሔርም ተስፋ ያደረግሁት
ሁሉ ሄዶአል" አልሁ።

19ዛይ፤ የጭንቀቴንና የመንከራተቴን፣
ምሬትንና ሐሞትን አስባለሁ።
20 ዘወትር አስበዋለሁ፤
ነፍሴም በውስጤ ተዋርዳለች።
21ሆኖም ይህን አስባለሁ
እንግዲያስ ተስፋ አለኝ፤

22ሔት፤ ያልጠፋነው *ከእግዚአብሔር* ታላቅ
ፍቅር የተነሣ ነው፤
ርኅራኄው አያልቅምና።
23ማለዳ ማለዳ አዲስ ነው፤
ታማኝነትህም ብዙ ነው።

[*1] የዚህ ምዕራፍ እያንዳንዱ አንጓ ተከታታይ ፊደላት ባሉት የዕብራይስጥ ሆሄያት የሚጀምር ሲሆን በእያንዳንዱ አንጓ ውስጥ ያሉት ጥቅሶች በአንድ ዐይነት ፊደል ይጀምራሉ።

2፥22 ኢዮ27፥14፤ መዝ31፥13፤ኤር11፥ 11፤20፥10፤ሆሴ9፥13
3፥1 ኢዮ19፥21፤ መዝ 88፥7፤ኤር15፥17-18
3፥2 ኢዮ19፥8፤መዝ 82፥5፤ኤር4፥23
3፥3 መዝ38፥2፤ኢሳ 5፥25
3፥4 ኢዮ30፥30፤ መዝ 51፥8፤ኢሳ38፥13፤ ኤር50፥17፤ሰቆ4፥8
3፥5 ቍ19፤ኤር 23፥15
3፥6 መዝ88፥5-6፤ 143፥3፤ኢሳ59፥10
3፥7 ኢዮ3፥23፤ ኤር40፥4
3፥8 ቍ44፤ዘዳ 1፥45፤ኢዮ30፥20፤ መዝ 5፥2፤22፥2
3፥9 ኢዮ9፥24፤ 19፥8፤ኢሳ63፥17፤ ሆሴ2፥6
3፥10 ኢዮ10፥16፤ ሆሴ 13፥8፤አሞ5፥18-19
3፥11 ሆሴ6፥1
3፥12 ኢዮ7፥20፤ 16፥12፤መዝ7፥12-13፤38፥2፤ሰቆ2፥4
3፥13 ኢዮ6፥4፤ 16፥13
3፥14 ዘፍ38፥23፤ ኢዮ17፥2፤30፥9፤ መዝ22፥6-7፤ኤር 20፥7
3፥15 ቍ19፤ኤር 9፥15
3፥16 መዝ7፥5፤ምሳ 20፥17
3፥18 ቍ54፤ኢዮ 17፥15
3፥19 ቍ5:15
3፥20 መዝ42፥5፡ 11፤43፥5
3፥22 ዘፀ78፥38፤ 130፥7፤103፥11፤ኢዮ 34፥15፤ሆሴ11፥9
3፥23 ዘፀ34፥6፤ሰፎ

2፥22 *በእኔ ላይ ጠራህ፤* 1፥15 ይመ፤ *ሽብርን ከየአቅጣጫው፤* የኤር6፥25 ማብ ይመ። *በእግዚአብሔር የቍጣ ቀን፤* ምዕራፉ በተጀመረበት መልክ ተደመደመ (ቍ1 ይመ)። *ማንም አላመለጠም ወይም አልተረፈም፤* ኤር42፥17፤44፥14 ይመ።

3፥1-2 *እኔ ነኝ፤* ጸሓፊው ኤርምያስም ሐዘን የተሰማው ሌላ ያልታወቀ ጸሓፊ እዚህ ላይ የሚናገረው ስለ ራሱ ብቻ ሳይሆን ተካፋይ ስለ ሆነበት ማኅበረ ሰብ መከራም ጭምር ነው፤ ("እኛ" የሚለውን በቍ22:40-47 ላይ ይመ)። በዕብራይስጥ ቋንቋ በተጻፈው ቅጅ ውስጥ ቍ1 በመጽሐፉ አጋማሽ ላይ ይገኛል።

3፥1 *በቍጣው፤* የእግዚአብሔር ማለት ነው። *በቍጣው በትር፤* ኢዮ 9፥34፤ 21፥9 ይመ፤ የሚያመለክተው ባቢሎንን ነው (ኢሳ 10፥5 ማብ ይመ)። *መከራ፤* ቍ19 ይመ።

3፥4 *አስረጀ፤* ኢዮ13፥28 (እንደሚጠፋ)፤ መዝ49፥14 (እንደሚያረጅ) ይመ። *ዐጥንቶቼንም ሰባበረ፤* ኢሳ38፥13 እና ማብ ይመ።

3፥5 *በምሬት፤* በቀጥታ ሲተረጐም "መርዝ" ማለት ነው (ኤር8፥14 እና ማብ ይመ)።

*3፥6፤* መዝ143፥3 የሚያስታውስ ነው። *በጨለማ፤* መቃብር ማለት ነው።

3፥7 *በቅጥር ... ዘጋብኝ፤* ይህን ትርጉም የሚሰጠው የዕብራይስጥ ቃልና በቍ 9 ላይ፣ "ዘጋ" የሚለውን ቃል የሚወክለው የዕብራይስጥ ቃል አንድ ነው (ኢዮ19፥8፤ ሆሴ2፥6 ይመ)። *ማምለጥ አልቻልሁም፤* መዝ88፥8 ይመ።

3፥8 *ጸሎቴን መስማት አልፈለገም፤* ቍ44፤ መዝ 18፥41፤ ምሳ 1፥28 ይመ፤ ኤር 7፥16 እና ማብ ይመ።

3፥9 *በተጠረቡ ድንጋዮች፤* በሰሎሞን ቤተ መቅደስ የመሠረት ሥራ ላይ እንደዋሉት ዐይነት ያሉ ትላልቅ ድንጋዮች ማለት ነው (1ነገ5፥17 ይመ)። *አጣመመ፤* ወይም፣ "አፈራረሰው አጠፋው" ማለት ነው (በኢሳ24፥1 ላይ እንዳለው ሁሉ)። ምስያው ምን እንደ ሆነ ለመገንዘብ ኢዮ30፥13 ይመ።

3፥10፤ *እንደ ... ድብ፣ እንደ ... አንበሳ፤* መዝ10፥9፤ 17፥12፤ ኤር4፥7፤ 5፥6፤ 49፥19፤ 50፥44 ይመ።

*3፥11፤* 1፥2ይመ

3፥12 *ቀስቱን ገተረ፤* የ2፥4 ማብ ይመ። *ዒላማ አደረገኝ፤* የኢዮ6፥4 ማብ ይመ።

3፥13 ልቤን፤ በቁሙ ሲተረጐም ኵላሊት ማለት ነው (ኢዮ 16፥13)።

*3፥14፤* የኤርምያስን ማማረር በኤር20፥7 ላይ ይመ። *በመሣለቅ ያዜሙብኛል* ቍ63፤መዝ69፥12 ይመ።

3፥15 *መራራ ሥር አበላኝ፤* በኢዮ9፥18 ላይ በዕብራይስጥ አጽንዖት የተሰጠው የዚህ ሐረግ ትርጕም፣ "በሐዘን ከበበኝ" እንደ ማለት ነው (የኤር9፥15 ማብ ይመ)። የፋሲካ ምግብ በሚበላበት ወቅት የመራራው አትክልት ተገቢነት ምን ያህል እንደ ሆነ ለማስተዋል የዘፀ12፥8 ማብ ይመ።

3፥18 *ከእግዚአብሔርም፤* በም3 ላይ አምላክ ለመጀመሪያ ጊዜ መጠቀሱ ነው።

*3፥19፤* ባለቅኔው እነዚህን ሁሉ የሕይወት ተሞክሮች በማስታወስ አሁንም በድጋሚ ይገልጻል። *ጭንቀቴንና መንከራተቴን፤* 1፥7 ይመ።

*3፥21-26፤* በሰቈቃወ ኤርምያስ መጽሐፍ ላይ በትምህርተ መለኮት ረገድ ከፍተኛ ሐሳብ የተገለጸበት ክፍል ነው (በመግቢያው ላይ፣ "ዐቢይ ሐሳብና ትምህርተ መለኮት" የሚለውን ይመ)።

3፥22 *ያልጠፋነው፤* የቍ1-2 ማብ ይመ። *ታላቅ ፍቅር፤* ቍ32 ይመ። በዕብራይስጥ ይህ ሐረግ ብዙ ቍጥር ሲሆን፣ (በመዝ107፥43 እንዳለው ማለት ነው)፣ ጌታ ለኪዳኑ ተስፋ ያለውን ታማኝነት የሚያመለክት ነው (መዝ89፥1 ይመ)። የመዝ6፥4 ማብ ይመ፤ እንዲሁም በኢሳ63፥7 ላይ፣ "ቸርነት" የሚለውንና ማብ ይመ።

3፥23 *ማለዳ ማለዳ፤* ኢሳ33፥2 ይመ። *ታማኝነትህም ብዙ ነው፤* ሊለካ እንደማይችል ያመለክታል (የ32 ማብ፤ እንዲሁም

[24]ራሴን እንዲህ አልሁት፤ "እግዚአብሔር
ዕድል ፈንታዬ ነው፤
ስለዚህ ተስፋ አደርገዋለሁ::

[25]ጤት፤ እርሱን ተስፋ ለሚያደርጉት፣
ለሚፈልገውም ሰው እግዚአብሔር
መልካም ነው::
[26]ሰው የእግዚአብሔርን ማዳን፣
ዝም ብሎ ተስፋ ቢያደርግ መልካም
ነው::
[27]ሰው በወጣትነቱ፣
ቀንበር ቢሸከም መልካም ነው::

[28]ዮድ፤ ብቻውን ዝም ብሎ ይቀመጥ፤
እግዚአብሔር አሸክሞታልና::
[29]ፊቱን በዐቧራ ውስጥ ይቅበር፤
ተስፋ ሊኖር ይችላልና::
[30]ጒንጩን ለሚመታው ሰው ይስጥ፤
ውርደትንም ይጥገብ::

[31]ካፍ፤ እግዚአብሐር ሰውን፣
ለዘላለም አይጥልምና፤
[32]መከራን ቢያመጣ እንኳ ይራራል፤
ታላቅ ፍቅሩ አይለወጥምና
[33]ሆን ብሎ ችግርን፣
ወይም መከራን በሰው ልጆች ላይ
አያመጣምና::

[34]ላሜድ፤ የምድሪቱ እስረኞች ሁሉ፣
በእግር ሲረገጡ፣
[35]በልዑል ፊት፣
ሰው መብቱ ሲነፈገው፣
[36]ሰው ፍትሕ ሲጓደልበት፣
ጌታ እንዲህ ዐይነቱን ነገር አያይምን?

[37]ሜም፤ እግዚአብሐር ካላዘዘ በቀር፤
ተናግሮ መፈጸም የሚችል ማን ነው?

[38]ክፉም ሆነ መልካም ነገር፣
ከልዑል አፍ የሚወጣ አይደለምን?
[39]ታዲያ ሕያው ሰው በኀጢአቱ ሲቀጣ፣
ስለምን ያጕረመርማል?

[40]ኖን፤ መንገዳችንን እንመርምር፤
እንፈትን፤
ወደ እግዚአብሔርም እንመለስ::
[41]ልባችንን ከእጃችን ጋር
በሰማይ ወዳለው ወደ አምላካችን
እናንሣ፤ እንዲህም እንበል፤
[42]"ዐምፀናል፤ ኀጢአትም ሠርተናል፤
አንተም ይቅር አላልኸንም::

[43]ሳሜኬት፤ "ራስህን በቍጣ ከደንህ፤
አሳደድኸንም፤
ያለ ርኅራኄም ገደልኸን::
[44]ጸሎት እንዳያልፍ፣ ራስህን በደመና
ሸፈንህ::
[45]በአሕዛብ መካከል፣
አተላና ጥራጊ አደረግኸን::

[46]ዔ፤ "ጠላቶቻችን ሁሉ፣
አፋቸውን በእኛ ላይ ከፈቱ::
[47]በጥፋትና በመፈራረስ፣
በችግርና በሽብር ተሠቃየን::
[48]የእንባ ጐርፍ ከዐይኔ ፈሰሰ፤
ሕዝቤ አልቋልና::

[49]ፌ፤ ያለ ዕረፍት፣
ያለ ማቋረጥ ዐይኖቼ እንባ ያፈሳሉ፤
[50]እግዚአብሔር ከላይ፣
ከሰማይ እስኪያይ ድረስ::

3፥5
3፥24 መዝ119፥57
3፥25 መዝ33፥18፤ ኢሳ 25፥9፤30፥18
3፥26 መዝ37፥7፤ 40፥1፤ኢሳ7፥4
3፥28 ኤር15፥17፤ ሰቆ2፥10
3፥29 ኢዮ2፥8፤ ኤር31፥17
3፥30 ኢዮ16፥10፤ ኢሳ50፥6፤ሚክ5፥1
3፥31 መዝ94፥14፤ ኢሳ54፥7
3፥32 መዝ78፥38፤ 106፥43-45፤ሆሴ 11፥8፤ ናሆ1፥12
3፥33 ኢዮ37፥23፤ ኤር31፥20፤ሕዝ18፥ 23፤ 33፥11
3፥35 ዘፍ14፥18፡ 19፡20፡22
3፥36 መዝ140፥12፤ ምሳ17፥15፤ኤር22፥3 ፤ዕን1፥13
3፥37 መዝ33፥9-11፤ ምሳ19፥21፤21፥30
3፥38 ኢዮ2፥10፤ ኢሳ45፥7፤ኤር32፥42
3፥39 ኤር30፥15፤ ሚክ7፥9
3፥40 መዝ119፥59፤ 139፥23-24፤2ቆሮ 13፥5
3፥41 መዝ25፥1፤ 28፥2
3፥42 2ነገ24፥4፤ ኤር5፥7-9፤14፥20፤ ዳን9፥5
3፥43 ቍ66፤መዝ 35፥6፤ሰቆ2፥2፡17፡21
3፥44 ቍ8፤መዝ 97፥2፤ኢሳ58፥4፤ሰቆ 2፥1፤ዘካ7፥13
3፥45 1ቆሮ4፥13
3፥46 መዝ22፥13፤ ሰቆ2፥16

3፥47 ኢሳ24፥17-18፤51፥19፤ኤር48፥43 3፥48 መዝ119፥136፤ ኤር9፥1፡18፤ሰቆ1፥16፤2፥11 3፥49 ኤር14፥17፤ሰቆ2፥18 3፥50 መዝ 14፥2፤80፥14፤ኢሳ63፥15

መዝ36፥5 ይመ):: *ታማኝነትህም፤* የጌታን ታላቅ ፍቅርና ቸርነት (ቍ22) ያመለክታሉ::

3፥24 *እግዚአብሔር ዕድል ፈንታዬ ነው፤* መዝ 73፥26፤ 142፥5 ይመ፤ የሌዋውያኑና የካህናቱ ርስት ድርሻ ጌታ ራሱ ነበር (ዘኍ18፥20፤ እንዲሁም የዘፍ15፥1 ማብ ይመ):: *ስለዚህ ተስፋ አደርገዋለሁ፤* ይህንን ሐረግ እንዲሁም በቍ21 ላይ፣ "ስለ ዚህ ተስፋ አደርጋለሁ" የሚወከለው የዕብራይስጡ አቻ ተመሳ ሳይ ሲሆን፣ እንደ አዝማች ያገለግላል::

3፥25 *እርሱን ተስፋ ለሚያደርጉት፤* መዝ25፥3፤ 69፥7 ይመ:: *እግዚአብሔር መልካም ነው፤* መዝ34፥8፤ 86፥5 ይመ::

*3፥26፤* ኢሳ26፥3፤30፥15 ይመ::

3፥27 *ሰው ... ቀንበር ቢሸከም፤* በቍ1ላይ፣ "መከራን ያየ ሰው" የሚለውን ሐሳብ ያስተጋባል::

3፥28 *ብቻውን ... ይቀመጥ፤* የ1፥1 ማብ ይመ:: *አሸክሞ ታልና፤* ቀንበሩን ማለት ነው (ቍ27 ይመ)::

3፥29 *ተስፋ ሊኖር ይችላልና፤* ኢዮ11፥18 ይመ::

3፥30 *ጒንጩን ... ይስጥ፤* ማቴ5፥39 ይመ:: *ውርደትንም ይጥገብ፤* መዝ123፥4 ይመ::

*3፥31፤* ኤር3፥5 እና ማብ ይመ::

*3፥32፤* የሚፈርደው ያው አምላክ እርሱ መልሶ ምሕረትን ይሰጣል (ኢዮ5፥18፤መዝ30፥5፤ኢሳ54፥8 ይመ):: *ታላቅ ፍቅሩ አይለወጥምና፤* የቍ22 ማብ ይመ:: እንዲሁም በቍ23 ላይ "ታማ ኝነትህ ታላቅ ነው" የሚለውንም ይመ፤ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ያለውን ኪዳናዊ ምሕረት በጥቅሉ ለማመልከት፣ ታማኝነትና የማ ይለወጥ ፍቅር ብዙውን ጊዜ በአንድ ላይ ይጠቀሳሉ::

3፥33 *ሆን ብሎ ችግርን ... አያመጣምና፤* ሕዝ18፥23፡32፤ ሆሴ11፥8፤ 2ጴጥ3፥9 ይመ::

3፥34 *በእግር ሲረገጡ፤* በ586 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎናውያን እንደ ፈጸሙት ሁሉ ማለት ነው::

3፥35 *ልዑል፤* የዘፍ 14፥19 ማብ ይመ:: *በልዑል ፊት፤* ፍትሕን ይበይኑ ዘንድ ልዑል እግዚአብሔር በሾማቸው ዳኞች ፊት ማለት ነው (ዘፀ22፥8-9፤ እንዲሁም አማራጭ ትርጒሙን፤ የመዝ 82 መግቢያ ይመ):: *መብቱ ሲነፈገው፤* የአይሁድ መሪዎች ሕግን በቀጥታ በመተላለፍ እንዳደረጉት ሁሉ ማለት ነው (ዘፀ 23፥6 ይመ)::

3፥36 *ፍትሕ ሲጓደልበት፤* ሰዎች ፍርድን ሊያጓድሉ ይች ላሉ፤ እግዚአብሔር ግን ከቶ አያደርገውም (ኢዮ8፥3፤34፥12 ይመ)::

3፥37 *ተናግሮ መፈጸም፤* የዘፍ1፥3 ማብ ይመ::

*3፥38፤* አሞ3፥6 ይመ::

3፥39 *ያጕረመርማል?* እስራኤላውያን በምድረ በዳ እንዳደረጉት ሁሉ ማለት ነው (ዘኍ11፥1 ይመ)::

3፥40 *መንገዳችንን እንመርምር፤* 1ቆሮ 11፥28 ይመ:: *ወደ እግዚአብሔርም እንመለስ፤* ሕዝቡ ወደ ጌታ እንዲመለሱ፣ ለቃ ሉም እንዲታዘዙ እንዲሁም እውነተኛ የልብ ለውጥ እንዲያሳዩ ነቢዩ ከሕዝቡ ጋር ራሱን እንደ አንዱ አድርጎ ይመለከታል የቍ1-2 ማብ ይመ:: ይህን ካደረጉ እግዚአብሔር ይሰማቸዋል፤ ይቤዣቸዋልም (ቍ55-58)::

3፥41 *ከእጃችን ... እናንሣ፤* የ2፥19 ማብ ይመ:: *በሰ ማይ፤* እግዚአብሔር በዙፋኑ ያለበት ስፍራ ነው (መዝ2፥4 ይመ)::

3፥42 *ዐምፀናል፤ ኀጢአትንም ሠርተናል፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነውን ንስሓ ለማስተዋል መዝ106፥6፤ ዳን 9፥5 ይመ::

3፥43 *በቍጣ ... አሳደድኸንም፤* ቍ66፤ኤር29፥18 ይመ:: *ያለ ርኅራኄም ገደልኸን፤* 2፥21 ይመ::

*3፥46፤* የ2፥16 ማብ ይመ::

3፥48 *የእንባ ጐርፍ ከዐይኔ ፈሰሰ፤* የ1፥16 ማብ ይመ:: *ሕዝቤ፤* የ2፥11 ማብ ይመ::

[51]በከተማዬ ባሉት ሴቶች ሁሉ ላይ
የደረሰውን ማየቴ፣
ነፍሴን አስጨነቃት::
[52]ጻዴ ያለ ምክንያት ጠላቶቼ የሆኑ፣
እንደ ወፍ አደኑኝ::
[53]ሕይወቴን በጕድጓድ ውስጥ ሊያጠፉ
ሞከሩ፣
ድንጋይም በላዬ አደረጉ::
[54]ውሃ ሞልቶ በዐናቴ ላይ ፈሰሰ፤
ጠፍቻለሁ ብዬ አሰብሁ::
[55]ቆፍ በጥልቁ ጕድጓድ ውስጥ ሳለሁ፣
እግዚአብሔር ሆይ፤ የአንተን ስም
ጠራሁ::
[56]ልመናዬን ሰምተሃል፤ "ርዳታም ፈልጌ
ስጮኽ፣
ከመስማት ጆሮህን አትከልክል::"
[57]በጠራሁህ ጊዜ ቀረብኸኝ፣
እንዲሁም፣ "አትፍራ" አልኸኝ::
[58]ሬስ ጌታ ሆይ፤ ለእኔ ተሟገትኸልኝ፤
ሕይወቴንም ተቤዠህ::
[59]እግዚአብሔር ሆይ፤ በእኔ ላይ
የተደረገውን ግፍ አየህ፤
ፍርዴን ፍረድልኝ!
[60]በቀላቸውን ሁሉ፣
በእኔም ላይ ያሰቡትን ዐድማ አየህ::
[61]ሳን እግዚአብሔር ሆይ፤ ስድባቸውን
ሁሉ፣
በእኔ ላይ ያሰቡትን ዐድማ ሁሉ ሰማህ፤
[62]ይህም ቀኑን ሙሉ በእኔ ላይ፣
ጠላቶቼ የሚያውጠነጥኑትና
የሚያንሾካሹኩት ነው::
[63]ተመልከታቸው! ቆመውም ሆነ
ተቀምጠው፣
በዘፈናቸው ይሣለቁብኛል::
[64]ታው እግዚአብሔር ሆይ፤ እጆቻቸው
ላደረጉት፣
የሚገባውን መልሰህ ክፈላቸው::
[65]በልባቸው ላይ መጋረጃን ዘርጋ፤
ርግማንህም በላያቸው ይሁን!
[66]ከእግዚአብሔር ሰማያት በታች፣
በቍጣህ አሳድዳቸው፤ አጥፋቸውም::

# 4

[*1]አሌፍ ወርቁ እንዴት ደበሰ!
ንጹሑስ ወርቅ እንዴት ተለወጠ!
የከበሩ ድንጋዮች፣
በየመንገዱ ዳር ተበታትነዋል::
[2]ቤት እንደ ወርቅ ይቈጠሩ የነበሩ፣
የከበሩ የጽዮን ወንዶች ልጆች፣
የሸክላ ሠሪ እጅ እንደ ሠራው፣
እንዴት አሁን እንደ ሸክላ ዕቃ ሆኑ!
[3]ጋሜል ቀበሮዎች እንኳን ግልገሎቻቸውን
ለማጥባት፣
ጡታቸውን ይሰጣሉ፤
ሕዝቤ ግን በምድረ በዳ እንዳሉ ሰጎኖች፣
ጨካኞች ሆኑ::
[4]ዳሌት ከውሃ ጥም የተነሣ፣
የሕፃናት ምላስ ከላንቃቸው ጋር
ተጣበቀ፤
ልጆቹ ምግብ ለመኑ፤
ነገር ግን ማንም አልሰጣቸውም::
[5]ሄ ምርጥ ምግብ ይበሉ የነበሩ፣
ተቸግረው በየመንገዱ ላይ ተንከራተቱ፤
ሐምራዊ ግምጃ ለብሰው ያደጉ፣
አሁን በዐመድ ክምር ላይ ተኙ::
[6]ዋው በሕዝቤ ላይ የደረሰው ቅጣት፣
የማንም እጅ ሳይረዳት፣
በድንገት ከተገለበጠችው፣
ሰዶም ላይ ከደረሰው ቅጣት ይልቅ
ታላቅ ነው::
[7]ዛይ መሳፍንቶቻቸው ከበረዶ ይልቅ
ብሩህ፣
ከወተትም ይልቅ ነጭ ነበሩ፤
ሰውነታቸው ከቀይ ዕንቍ የቀላ፣
መልካቸውም እንደ ሰንፔር[a] ነበር::
[8]ሔት አሁን ግን ከጥላሸት ይልቅ
ጠቍረዋል፤

3፥52 መዝ35፥7
3፥53 ኤር37፥16፤ 38፥6
3፥54 ቍ18፤መዝ 69፥2፤88፥5፤ሕዝ37፥11፤ዮና2፥3-5
3፥55 መዝ88፥6፤ 130፥1፤ዮና2፥2
3፥56 መዝ55፥1፤ 116፥1-2
3፥57 መዝ46፥1፤ ኢሳ41፥10
3፥58 መዝ34፥22፤ ኤር50፥34፤51፥36
3፥59 መዝ35፥23፤ 43፥1፤ኤር18፥19-20
3፥60 ኤር11፥20፤ 18፥18
3፥61 መዝ89፥50፤ ሰፎ2፥8
3፥62 መዝ36፥3
3፥63 ኢዮ30፥9
3፥64 መዝ28፥4፤ ኤር51፥6
3፥65 ዘፀ14፥8፤ ዘዳ2፥30፤ኢሳ6፥10
3፥66 ቍ43
4፥1 ሕዝ7፥19
4፥2 ኢሳ51፥18
4፥3 ኢዮ39፥16
4፥4 ዘዳ28፥48፤ 2ነገ18፥31፤መዝ22፥15፤ሰቆ2፥11:12
4፥5 ኢሳ3፥26፤ኤር 6፥2፤አሞ6፥3-7
4፥6 ዘፍ19፥25

*1 ይህ ምዕራፍ፣ ጥቅሶቹ ተከታታይ ፊደላት ባሉት የዕብራይስጥ ሆሄያት የሚጀምር ቃል ወይም ዐረፍተ ነገር ያለው ግጥም ነው::
[a]7 ወይም ላፒስ ላዙሊ

3፥51 *በከተማዬ ባሉት ሴቶች፤* 1፥4:18፤2፥20-21፤5፥11 ይመ::
3፥52 *ያለ ምክንያት ጠላቶቼ፤* የመዝ35፥19 ማብ ይመ፤ *እንደ ወፍ፤* መዝ11፥1 ይመ::
3፥53 *ድንጋይም በላዬ አደረጉ፤* ዘሌ20፥2:27፤1ነገ12፥18 ይመ::
3፥54 *ውሃ ሞልቶ በዐናቴ ላይ ፈሰሰ፤* የመዝ42፥7 ማብ ይመ:: *ጠፍቻለሁ፤* መዝ31፥22፤ኢሳ53፥8 ይመ::
3፥55 *በጥልቁ ጕድጓድ፤* የመዝ30፥1 ማብ ይመ::
3፥56 *ርዳታም ፈልጌ፤* ኢዮ32፥20፤መዝ118፥5 ይመ::
3፥57 *በጠራሁህ ጊዜ ቀረብኸኝ፤* መዝ145፥18 ይመ:: *አትፍራ፤* ኤርምያስ ትንቢት እንዲናገር የተጠራበትን የሚያስታውስ ነው (ኤር1፥8 እና ማብ ይመ)::
3፥58 *ሕይወቴንም ተቤዠህ፤* መዝ103፥4 እንዲሁም የመዝ 25፥22 ማብ ይመ::
3፥63 *ቆመውም ሆነ ተቀምጠው፤* ማንኛውንም ተግባር እያከናወኑ ሳለ (ዘዳ6፥7፤11፥19፤መዝ139፥2፤ኢሳ37፥28 ይመ):: *በዘፈናቸው ይሣለቁብኛል፤* የቍ14 ማብ ይመ::
3፥64 ከመዝ28፥4 ጋር አቻ ነው፤ የመዝ5፥10 ማብ ይመ::
3፥65 *በልባቸው ላይ መጋረጃን፤* 2ቆሮ3፥15 ይመ:: *ርግማንህም በላያቸው ይሁን፤* ከመዝ3፥8 ጋር ያነጻጽሩ::
4፥1 *እንዴት ... !* የ1፥1 ማብ ይመ:: *ወርቅ ... ድንጋዮች፤* በትእምርትነት የእግዚአብሔርን ሕዝብ ያመለክታሉ (ቍ2 ይመ):: ምስያው ምን እንደሚመስል ለማስተዋል ማሕ5፥11-12: 14-15፤ ዘካ9፥16 ይመ:: *ደበሰ፤* በቁሙ መልኩን አጣ ማለት ነው ከሚል3፥6 ጋር ያነጻጽሩ:: *በየመንገዱ ዳር፤* 2፥19፤ ኢሳ 51፥20 ይመ::
4፥2 *እንደ ወርቅ ይቈጠሩ፤* ኢዮ28፥15-19 ይመ:: *የሸክላ ሠሪ እጅ ... እንደ ሸክላ ዕቃ፤* ኢሳ45፥9፤60፥21 እና ማብ ይመ::
4፥3 *ሕዝቤ፤* ቍ6:10፤ እንዲሁም የ2፥11 ማብ ይመ::
4፥5 *ምርጥ ምግብ ... ሐምራዊ፤* ዘፍ49፥20 ይመ:: ሐምራዊ የቤተ መንግሥት ሰው የሚለብሰው ልብስ የለም ነበር (ለምሳሌ መሳ8፥26፤ እንዲሁም የማሕ7፥5 ማብ ይመ):: *በየመንገዱ ላይ ተንከራተቱ፤* የ1፥13 ማብ ይመ::
4፥6 *በሕዝቤ፤* የ2፥11 ማብ ይመ:: *በድንገት ከተገለበጠችው፤* ለረጅም ጊዜ በወራሪዎች በመከበብ ከሚደርስ ሥቃይ ተርፋለች (እንደ ኢየሩሳሌም ማለት ነው):: ወረራ ከሚያስከትለው ሥቃይ ድናለች:: *ሰዶም፤* የኤር 20፥16 ማብ ይመ::
4፥7 *ነጭ ... የቀላ፤* በዕብራይስጥ አጽንዖት የተሰጣቸው ከነዚህ ሁለት ቃሎች፣ "የሚያንጸባርቅ...የቀላ" በማለት በማሕ5፥10 ተተርጕመዋል:: *ከቀይ ዕንቍ፤* ኢዮ28፥18 ይመ:: *ሰንፔር፤* ማሕ 5፥14 እና ማብ፤ ኢሳ 54፥11እና ማብ ይመ::

በመንገድም የሚያውቃቸው የለም፤
ቆዳቸው ከዐጥንታቸው ጋር ተጣብቆአል፤
እንደ ዕንጨትም ደርቀዋል።

9ጤት፤ በራብ ከሚሞቱት ይልቅ፣
በሰይፍ የተገደሉት ይሻላሉ፤
ምግብ በሜዳ ላይ ካለማግኘታቸው የተነሣ፣
በራብ ደርቀው ያልቃሉ።

10ዮድ፤ ሕዝቤ ባለቀበት ጊዜ፣
ምግብ እንዲሆኑአቸው፣
ርኅሩኆቹ ሴቶች በገዛ እጆቻቸው፣
ልጆቻቸውን ቀቀሉ።

11ካፍ፤ *እግዚአብሔር* ለመቅሠፍቱ መውጫ
በር ከፈተ፤
ጽኑ ቍጣውን አፈሰሰ፤
መሠረትዋን እንዲበላ፣
በጽዮን እሳት ለኰሰ።

12ላሜድ፤ ጠላቶችም ሆኑ ወራሪዎች፣
የኢየሩሳሌምን በሮች ጥሰው
ይገባሉ ብለው፣
የምድር ነገሥታት፣
ወይም ከዓለም ሕዝብ አንዳቸውም
አላመኑም።

13ሜም፤ ይህ ግን ከነቢያት ኀጢአት፣
ከካህናቷም መተላለፍ የተነሣ
ሆኖአል፤
በውስጧ፣
የጻድቃንን ደም አፍስሰዋልና።

14ኖን፤ እንደ ታወሩ ሰዎች፣
በየመንገዱ ላይ ይደናበራሉ፤
ማንም ሰው ደፍሮ ልብሳቸውን መንካት
እስከማይችል ድረስ፣
በደም እጅግ ረክሰዋል።

15ሳምኬት፤ ሰዎች "ሂዱ! እናንት ርኩሳን!"
ብለው ይጮኹባቸዋል፤
"ወግዱ! ወግዱ! አትንኩን!"
ይሏቸዋል፤
ሸሽተው በሚቅበዘበዙበትም ጊዜ፣
በአሕዛብ መካከል ያሉ ሰዎች፣
"ከእንግዲህ በዚህ መቀመጥ አይ
ገባቸውም!" ይላሉ።

16ፌ፤ *እግዚአብሔር* ራሱ በትኖአቸዋል፤
ከእንግዲህ ወዲያ አይጠብቃቸውም፤
ካህናቱ አልተከበሩም፤
ሽማግሌዎቹም ከበሬታ አላገኙም።

17ጻዴ፤ ከሁሉም በላይ በከንቱ ርዳታን
ስንጠባበቅ፣
ዐይኖቻችን ደከሙ፤
ከግንብ ማማችን ላይ ሆነን፣
ሊያድን ከማይችል ሕዝብ ርዳታ
ጠበቅን።

18ቆፍ፤ ሰዎች እግር እግራችንን
ተከታተሉን፤
ስለዚህ በመንገዳችን መሄድ
አልቻልንም፤
መጨረሻችን ቀርቦአል፤ ቀኖቻችንም
ተቈጥረዋል፤
ፍጻሜያችን መጥቶአልና።

19ሬስ፤ ከሰማይ ንስሮች ይልቅ፣
ጠላቶቻችን ፈጣኖች ናቸው፤
በተራሮች ላይ አሳደዱን፤
በምድረ በዳም ሸመቁብን።

20ሺን፤ በእግዚአብሔር የተቀባው፣
የሕይወታችን እስትንፋስ፣
በወጥመዳቸው ተያዘ፤
በጥላው ሥር፣
በአሕዛብ መካከል እንኖራለን ብለን
አስበን ነበር።

21ታው፤ አንቺ በዖፅ ምድር የምትኖሪ፣
የኤዶምያስ ሴት ልጅ ሆይ፤ ደስ
ይበልሽ፤ ሐሴትም አድርጊ!
ነገር ግን ለአንቺም ደግሞ ጽዋው
ይደርስሻል፤
ትሰክሪያለሽ፤ ዕርቃንሽንም
ትጋለጫለሽ።

22ታው፤ የጽዮን ልጅ ሆይ፤ ቅጣትሽ
ያበቃል፤
እርሱም የስደትሽን ዘመን አያራዝምም፤
ነገር ግን አንቺ የኤዶምያስ ልጅ ሆይ፤
ኀጢአትሽን ይቀጣል፤
ከፋትሽንም ይፋ ያወጣል።

## 5

*እግዚአብሔር* ሆይ፤ በእኛ ላይ
የደረሰውን አስብ፤
ውርደታችንን እይ፤ ተመልከትም።

4፥8 ኢዮ30፥28፤ መዝ 102፥3-5፤ ሰቆ3፥4
4፥9 2ነገ25፥3፤ኤር 15፥2፤16፥4፤ሰቆ5፥10
4፥10 ዘሌ26፥29፤ ዘዳ 28፥53-57፤ኤር 19፥9፤ ሰቆ2፥20፤ሕዝ 5፥10
4፥11 ዘዳ32፥22፤ 2ዜና 34፥21፤ኢዮ 20፥23፤ኤር7፥20፤17 ፥27፤ሕዝ22፥31፤ናሆ 1፥6፤ሶፎ2፥2፤3፥8
4፥12 1ነገ9፥9፤ኤር 21፥13
4፥13 2ነገ21፥16፤ ኤር5፥31፤6፥13፤ሕ ዝ22፥28፤ሚክ3፥11
4፥14 ኢሳ59፥10፤ ኤር19፥4
4፥15 ዘሌ13፥46፤ ኤር44፥14፤ሚክ2፥10
4፥16 ኢሳ9፥14-16፤ ሰቆ2፥6፤5፥12
4፥17 ዘፍ15፥18፤ኢሳ 20፥5፤ኤር37፥7፤ሰቆ 1፥7፤ሕዝ29፥16
4፥18 ሕዝ7፥2-12፤ አሞ8፥2
4፥19 ዘዳ28፥49፤ ዘሌ 26፥36፤ኢሳ5፥ 26-28፤ኤር52፥7
4፥20 1ሳሙ26፥9፤ 2ሳሙ19፥21፤መዝ91 ፥1፤ኤር39፥5፤ሕዝ 12፥12-13፤19፥4፡8
4፥21 ዘፍ10፥23፤ መዝ16፥5፤ኢሳ34፥6- 10፤63፥6፤ኤር25፥15 ፤ሕዝ35፥15፤ አሞ1፥ 11-12፤አብ1፥16፤ዕን 2፥16
4፥22 መዝ137፥7፤ ኢሳ40፥2፤ኤር33፥ 8፤ሕዝ25፥12-14፤ ሚል1፥4
5፥1 መዝ44፥13- 16፤89፥50

4፥8 *ቆዳቸው ከዐጥንታቸው ጋር ተጣብቆአል፤* ኢዮ19፥20 ይመ።

*4፥10፤* የኤር19፥9 ግብ ይመ። *ሕዝቤ፤* የ2፥11 ግብ ይመ።

4፥11 *ጽኑ ቍጣውን፤* የ1፥12 ግብ ይመ። *እንዲበላ … እሳት ለኰሰ፤* የኤር17፥27 ግብ ይመ።

4፥12 *ሕዝብ፤* ወይም ገዥዎች (ነገሥታት ከሚለው ጋር ተመሳሳይ ነው)፤ በዕብራይስጥ አጽንዖት የተሰጠው ይህ ቃል በአሞ1፥5፡8 ላይ፣ "ንጉሥ" ተብሎአል።

4፥13 *ከነቢያት ኀጢአት፣ ከካህናቷም … የተነሣ፤* ኤር 26፥7-11፡16፤ ይመ፤ እንዲሁም ኤር 6፥13-15፤ 23፥11-12፤ ሕዝ 22፥26፡28 ይመ።

4፥14 *እንደታወሩ ሰዎች … ይደናበራሉ፤* ዘዳ28፥28-29፤ኢሳ 29፥9 እና ግብ፤ 59፥10 እና ግብ፤ ሶፎ1፥17 ይመ። *በደም… ረክሰዋል፤* ኢሳ59፥3 ይመ።

4፥15 *ሰዎች … ከእንግዲህ፤* ይህ አስፈሪ ሁኔታ በዘዳ28፥65-66 ተገልጸአል። *ርኩሳን፤* የቆዳ በሽታ ያለበት የሚያሰማው ጩኸት ነው (ዘሌ13፥45) ይመ።

*4፥16፤* ይህኛውም ማስደንገጫ በዘዳ28፥49-50 ተገልጸአል።

4፥17 *ዐይኖቻችን ደከሙ፤* ዘዳ28፥28፤ መዝ69፥3 ይመ። *ሊያድን ከማይችል ሕዝብ፤* ለምሳሌም ከግብፅ ማለት ነው (ሕዝ 29፥16 ይመ)።

4፥19 *ንስሮች፤* ኤር4፡13፤48፥40 እና ግብ ይመ። *በምድረ በዳም፤* የኢያሪኮ ሜዳ ማለት ነው (ኤር39፥5፤52፥8)።

4፥20 *በእግዚአብሔር የተቀባው፤* ንጉሥ ሴዴቅያስን ማለት ነው። *የሕይወታችን እስትንፋስ፤* በቀጥታ የአፍንጫችን ትንፋሽ ማለት ነው። *ተያዘ፤* ኤር39፥4-7፤52፥7-11 ይመ። *በጥላው፤* መከላከያ ማለት ነው። (የመሳ9፥15 ግብ ይመ)።

4፥21 *በዖፅ ምድር፤* ኤር25፥20፤ እንዲሁም የኢዮ1፥1 ግብ ይመ። *የኤዶምያስ፤* የኤር49፥8 ግብ ይመ። *ጽዋው፤* የኤር 25፥15 ግብ ይመ። *ዕርቃንሽንም ትጋለጫለሽ፤* 1፥8፤ እንዲሁም ኤር49፥10፤ ናሆ3፥5፤ ይመ።

4፥22 *የጽዮን ልጅ፤* የ1፥6 ግብ ይመ። *ከፋትሽንም ይፋ*

[2]ርስታችን ለመጻተኞች፣
ቤቶቻችን ለባዕዳን ዐልፈው ተሰጡ።
[3]ወላጅ አልባና አባት የሌላቸው ሆንን፤
እናቶቻችን እንደ መበለቶች ሆኑ።
[4]ለምንጠጣው ውሃ መክፈል ነበረብን፤
ዕንጨታችንንም የምናገኘው በግዢ
ነበር።
[5]የሚያሳድዱን ከተረከዞቻችን ሥር ናቸው፤
ተጨንቀናል ዕረፍትም አጥተናል።
[6]እንጀራ እንጠግብ ዘንድ፣
ለአሦርና ለግብፅ እጃችንን ሰጠን።
[7]አባቶቻችን ኀጢአት ሠርተው አለፉ፤
እኛም የእነርሱን ቅጣት ተሸከምን።
[8]ባሮች ሠልጥነውብናል፤
ከእጃቸው ነጻ የሚያወጣን ማንም
የለም።
[9]በምድረ በዳ ካለው ሰይፍ የተነሣ፣
በሕይወታችን ተወራርደን እንጀራ
አገኘን።
[10]ቈዳችን እንደ ምድጃ ጠቍሮአል፤
በራብም ተቃጥሎአል።
[11]ሴቶች በጽዮን፣
ደናግል በይሁዳ ከተሞች ተደፈሩ።
[12]መሳፍንት በእነርሱ እጅ ተሰቀሉ፤
ሽማግሌዎችም አልተከበሩም።
[13]ጕልማሶች ወፍጮ እንዲፈጩ ተገደዱ፤
ወንዶች ልጆች በዕንጨት ሸክም
ተንገዳገዱ።
[14]ሽማግሌዎች ከከተማዪቱ በር ሄደዋል፤
ጕልማሶች ዝማሬያቸውን አቁመዋል።
[15]ደስታ ከልባችን ጠፍቶአል፤
ጭፈራችን ወደ ልቅሶ ተለውጦአል።
[16]አክሊላችን ከራሳችን ላይ ወድቆአል፤
ወዮልን፤ ኀጢአት ሠርተናልና!
[17]ከዚህ የተነሣ ልባችን ደከመ፤
ከእነዚህ የተነሣም ዐይናችን ፈዘዘ፤
[18]ባዶዋን የቀረችው የጽዮን ተራራ፣
የቀበሮዎች መፈንጫ ሆናለችና።

[19]አቤቱ እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ
ለዘላለም ትገዛለህ፤
ዙፋንህ ከትውልድ እስከ ትውልድ
ይኖራል።
[20]ስለምን ፈጽመህ ትረሳናለህ?
ስለምንስ ለረዥም ጊዜ ትተወናለህ?
[21]እግዚአብሔር ሆይ፤ ወደ አንተ መልሰን፤
እኛም እንመለሳለን፤
ዘመናችንን እንደ ቀድሞው አድስ፤
[22]ፈጽመህ ካልጣልኸን፣
ከመጠን በላይ ካልተቈጣኸን።

5፥2 መዝ79፥1፤ 109፥11፤ኤር17፥4፤ ሰፎ1፥13
5፥3 ዘፀ22፥24፤ ኤር15፥8፤18፥21
5፥4 ኢሳ3፥1፤ኢሳ 55፥1፤ሕዝ4፥16-17
5፥5 ኢሱ1፥13፤ነህ 9፥37፤ኢሳ47፥6
5፥6 ኤር2፥36፤ሆሴ 5፥13፤7፥11፤9፥3
5፥7 ኤር14፥20፤ 16፥12፤31፥29
5፥8 ነህ5፥15፤ዘካ 11፥6
5፥10 ኢዮ30፥ 30፤ሰቆ4፥8-9
5፥11 ዘፍ34፥29፤ ዘካ14፥2
5፥12 ዘሌ19፥32፤ ሰቆ2፥6፤4፥16
5፥14 ኢሳ24፥8፤ ኤር7፥34
5፥15 ኤር25፥10፤ አሞ8፥10
5፥16 ኢዮ19፥9፤ መዝ89፥39፤ኢሳ3፥ 11፤ኤር13፥18፤14፥20
5፥17 ኢዮ16፥8፤ መዝ 6፥7፤ኢሳ1፥5፤ ኤር8፥18
5፥18 መዝ74፥2-3፤ ኢሳ27፥10፤ሚክ3፥12
5፥19 1ዜና16፥31፤ መዝ45፥6፤102፥12፡ 24-27
5፥20 መዝ13፥1፤ 44፥24፤71፥11
5፥21 መዝ80፥3፤ ኢሳ60፥20-22
5፥22 መዝ53፥5፤ 60፥1-2፤ ኢሳ64፥9፤ ኤር6፥30

*ያወጣል፤* ከመዝ32፥1፤85፥2 ጋር ያነጻጽሩ።

5፥2 *ርስታችን፤* የይሁዳ ምድር ማለት ነው (ኤር2፥7 እና ማብ እንዲሁም 3፥18 ይመ)።

5፥4 *ውሃ መክፈል ነበረብን፤ ዕንጨታችንንም፤* ከዘዳ 29፥11፤ ከኢሱ9፥21፡23፡27 ጋር ያነጻጽሩ። *ዕንጨታችንንም፤* የማገዶ ዕንጨት ነው።

5፥6 *ለአሦር፤* ይኸውም (1) በቍሙ አሦርን (ኤር2፥18 ይመ)፤ ወይም (2) ቀደም ብሎ በአሦር ተይዞ የነበረውን ግዛት ማለት ነው (የዕዝ 6፥22 ማብ ይመ)። *እጃችንን ሰጠን፤* 1ዜና 29፥24፤ 2ዜና30፥8፤ ኤር50፥15 እንዲሁም 2ነገ10፥15፤ ዕዝ10፥19፤ ሕዝ17፥18 ይመ።

*5፥7፤* በኢየሩሳሌም ላይ ለደረሰው መከራ አባቶችም ሆኑ ልጆች ኀላፊነት አለባቸው (ቍ16፤ኤር16፥11-12፤31፥29-30፤ሕዝ 18፥2-4 ይመ፤ ከኢሳ65፥7 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥8 *ባሮች፤* በዚህ ጊዜ ኢየሩሳሌምን በመግዛት ላይ ያሉትን ባቢሎናውያንን ምፀታዊ በሆነ ስልት ማመልከቱ ነው፤ (ኢየሩሳሌም ከግዛቶቹ ሁሉ ንግሥት ነበረች 1፥1)፤ ምሳ30፥21-22 ይመ።

5፥9 *በምድረ በዳ ካለው ሰይፍ፤* ለዝርፊያ የተሰማሩ ታጣቂዎች ናቸው።

5፥12 *ተሰቀሉ፤* ከግድያው በተጨማሪ የተፈጸመ አስጸያፊ ድርጊት ነው (ዘዳ21፥22-23 ማብ ይመ)።

5፥13 *ወፍጮ እንዲፈጩ፤* የውርደት ሥራ ነው (የመሳ 9፥53 ማብ እንዲሁም ኢሳ47፥2 ይመ)።

5፥14 *ከከተማዪቱ በር፤* የከተማዋ አደባባይ ነው (ኢሱ 20፥4 ይመ)፤ በተጨማሪም ለውይይትና ለግብግ የሚሰበሰቡበት ቦታ ነው (ከ1፥4 ጋር ያነጻጽሩ)።

*5፥15፤* ኤር7፥34፤ 16፥9፤ 25፥10 ይመ። ከመዝ30፥11፤ ከኤር 31፥13 ጋር ያነጻጽሩ።

5፥16 *አክሊላችን፤* የኢየሩሳሌምን ከተማ ሞገስና ክብር በትእምርትነት ያሳያል (1፥1፤2፥15 ይመ፤ ከኢሳ28፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥17 *ልባችን ደከመ፤* የ1፥22 ማብ ይመ። *ዐይናችን ፈዘዘ፤* 2፥11፤ እንዲሁም የመዝ6፥7 ማብ ይመ።

5፥18 የቀበሮዎች፤ መሳ15፥4 ማብ ይመ።

*5፥19፤* ከመዝ102፥12 ጋር ተመሳሳይ ነው (የዚሁ ማብ ይመ)።

5፥21 *መልሰን ... እንመለሳለን፤* ኤር31፥18 እንዲሁም የኤር31፥18-19 ማብ ይመ።

*5፥22፤* ኤር14፥19 ይመ። ተመሳሳዩ የሆነ አሳዛኝ አጨራረስ የሌሎች ሰቈቃዎች ባሕርይ ብቻ ሳይሆን (ለምሳሌ መዝ88) ፣ የአንዳንድ የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትም ባሕርይ ነው (ለምሳሌ ትንቢተ ኢሳይያስና ሚልክያስ)። ከዚህም የተነሣ ይኸው መጽሐፍ በይፋ በተነበበ ጊዜ ቍ22 ከተነበበ በኋላ ቍ21 ተደግሞ ይነበብ ነበር።

# ትንቢተ ሕዝቅኤል

## መግቢያ

### ታሪካዊ ዳራ

ነቢዩ ሕዝቅኤል የኖረው ዓለም አቀፍ ክብርና ነውጥ በነበረበት ዘመን ነው:: የሶርያንና የፓለስታይንን ይዞታ አሸንፎ የያዘውና በዓ.ቅ.ክ 722-721 የሰሜኑን የእስራኤል መንግሥት የደመሰሰው የአሦር መንግሥት፣ እንደ ገና ባንሠራራው በባቢሎን መንግሥት ጥቃት ስለደረሰበት መፈራረስ ጀመረ:: በዓ.ቅ.ክ 612 ታላቋ የአሦር ከተማ የነበረችው ነነዌ በተባበረው የባቢሎናውያንና የሜዶናውያን ሰራዊት ሥር ወደቀች:: ከሦስት ዓመት በኋላ የግብፅ ንጉሥ የነበረው ዳግማዊ ፈርዖን ኒካው አሦራውያንን ለመርዳትና ለዘመናት በፓለስታይንና በሶሪያ ላይ የነበረውን የግብፅን ተፅዕኖ እንደ ገና ለመመለስ ሙከራ አደረገ:: ንጉሥ ሕዝቅያስ እንዳደረገው ሁሉ የባቢሎን ተባባሪ የሆነው የይሁዳ ንጉሥ ኢዮስያስ በመጊዶ የግብፅን ሰራዊት እንቅስቃሴ ለመግታት ሞከረ፤ ነገር ግን ሕይወቱን አጣ፤ በጦርነቱም ተሸነፈ (2ነገ23፥29-30፤ 2ዜና35፥20-24 ይመ)::

የኢዮስያስ ልጅ ኢዮአክስ ይሁዳን ሦስት ወር ብቻ ገዛ፤ ከዚህም በኋላ ኒካው ሌላውን የኢዮስያስን ልጅ ኢዮአቄምን የግብፅ መንግሥት ተወካይ እንዲሆን ዓ.ቅ.ክ 609 በኢየሩሳሌም አነገሠው:: በዓ.ቅ.ክ 605 ባቢሎናውያን የግብፅን ሰራዊት በከርሚሽ ድል አደረጉት (ኤር46፥2)፤ ከዚያም ወደ ደቡብ እስከ ፍልስጥኤም ሜዳ ድረስ ገፉ:: በዚሁ ዓመት ናቡከደነፆር በባቢሎን ዙፋን ላይ ከፍ ከፍ አለ፤ ኢዮአቄምም ለእርሱ ታማኝ እንደሚሆን ገለጸ:: ይሁን እንጂ ከጥቂት ዓመታት በኋላ የግብፅና የባቢሎን ሰራዊት በደቡብ ምዕራብ ፓለስታይን ለመሸናነፍ ጦርነት ባደርጉ ጊዜ፣ ኢዮአቄም በአዲሱ ጌታው ላይ ዐመፀ::

በዚህ ጊዜ ናቡከደነፆር በዓ.ቅ.ክ. 597 ኢየሩሳሌምን ወግቶ የሚይዝ ሰራዊት በመላክ ፈጣን አፀፋዊ ምላሽ ሰጠ:: የኢዮአቄም ልጅ ዮአኪን እንዲሁም ሕዝቅኤልን ጨምሮ ዐሥር ሺህ አይሁድ ወደ ባቢሎን ተጋዙ፤ እዚያም በኢዮአቄም "ሦስተኛ ዓመት" (ዳን1፥1 እና ማብ ይመ) ወደ ባቢሎን ከተጋዙት ጋር ተጨመሩ:: ናቡከደነፆርም የዮአኪንን አጎት ሴዴቅያስን በኢየሩሳሌም በዙፋኑ ላይ አስቀመጠው፤ ይሁን እንጂ ሴዴቅያስም ቢሆን በአምስት ወይም ስድስት ዓመት ጊዜ ውስጥ ዐመፀ:: በዓ.ቅ.ክ. 588 ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምን ከበቡ፤ በዓ.ቅ.ክ. 586 በሐምሌ ወር የኢየሩሳሌም ቅጥሮች ተሰበሩ፤ ከተማዪቱም ተዘረፈች:: በዓ.ቅ.ክ. 586 ነሐሴ ዐሥራ አራት ቀን ከተማይቱና ቤተ መቅደስዋ ተቃጠሉ::

በዓ.ቅ.ክ. 539 በፋርሱ ንጉሥ በቂሮስ እስከ ተደመሰሰችበት ጊዜ ድረስ፣ ባቢሎን በናቡከደነፆርና ከእርሱ በኋላ በተነሡት መሪዎችም አማካይነት ዓለም አቀፋን ሁኔታ በሙሉ ትቈጣጠር ነበር::

የእስራኤል ንጉሣዊ አገዛዝ አከተመ፤ የዳዊት ከተማና የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስም አበቃለት::

### የትንቢቱ ጸሓፊ

ስለ ሕዝቅኤል የሚነገረው ሁሉ የተገኘው በስሙ ከሚጠራው መጽሐፍ ብቻ ነው:: በዓ.ቅ.ክ. 597 ናቡከደነፆር ወደ ባቢሎን ካፈለሳቸው አይሁድ መካከል አንዱ ነበር፤ እዚያም ለነቢይነት አገልግሎት በእግዚአብሔር ተጠራ (1፥1-3 ይመ):: ሕዝቅኤል ሚስት ነበረችው (24፥15-18)፤ በራሱ ቤት ይኖር ነበር፤ (3፥24፤ 8፥1 ይመ) አብረውት ከተሰደዱትም ጋር በመጠኑም ቢሆን የእንቅስቃሴ ነጻነት ነበረው::

ሕዝቅኤል ከካህናት ቤተ ሰብ ሲሆን፣ (በ1፥3 ላይ አማራጭ ትርጕሙን ይመ) ካህን ሆኖ ለማገልገልም የሚገባው ሰው ነበር:: የሕዝቡ ልዩ ምልክት ከሆነው፣ መሥዋዕቶች ከሚቀርቡበት፣ የካህናት አገልግሎትና የአምልኮ ሥርዓቶች ከሚካሄዱበት ከእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ የተቋረጡትንና የራቁትን ምርኮኞች ካህንም ነቢይም ሆኖ ለማገልገል ተጠራ፤ መልእክቱም በአብዛኛው ከቤተ መቅደስና ከሥርዓቶቹ ጋር የተያያዘ ነበር (በተለይ ም8-11 እና ም40-48 ይመ)::

ሕዝቅኤል የራሱን አገር ብሔራዊ ባህል ብቻ ሳይሆን፣ ዓለም አቀፋዊ ጉዳዮችንና ታሪክን ሁሉ የሚገነዘብ ሰፋ ያለ ዕውቀት ያለው ሰው ነበረ:: ከመርከብ ሥራ አንስቶ እስከ ሥነ ጽሑፍ ድረስ በአጠቃላይ ጕዳዮች ላይ የነበረውም ዕውቀት እጅግ የሚያስደንቅ ነው፤ ልዩ ዕውቀት የተሰጠውና ታላላቅ ጕዳዮችን ተረድቶ በተለየ መንገድ የመግለጽ ችሎታ የነበረው ሰው ነው:: የአገላለጽ ዘዴው አብዛኛውን ጊዜ የተለየና ሰማያዊ ቢሆንም የተለመደው አጻጻፉ ግን ስሜትን የሚነካና ተጨባጭ ነው (ም16 እና 23 ይመ)::

ከማንኛውም ነቢይ ይልቅ ራሱን ከመለኮታዊው ቃል ጋር በማዛመድ ትንቢቱን ትእምርታዊ በሆነ መንገድ በድርጊት አሳይቶአል::

### የተጻፈበት ሁኔታና ዓላማው

አብረውት ከነበሩት ምርኮኞች ጋር ሕዝቅኤል በባቢሎን ቢኖርም፣ ከተጠራበት መለኮታዊ ጥሪ የተነሣ ኢየሩሳሌም ከመፍረሷ በፊት ቀደም ብሎ የመመለሱን ፍላጎት ገታው:: በመጀመሪያዎቹ ሰባቱ የአገልግሎት ዓመታት 593-586 ዓ.ቅ.ክ አብረውት ለነበሩት አይሁድ በታማኝነት፣ አስፈሪውን፣ ልብ የሚሰነጥቀውንና ተስፋ አስቈራጩን መለኮታዊ የፍርድ ቃል ይኸውም የኢየሩሳሌምን መውደቅ እንደ

ገና ተናገረ (ም1-24 ይመ)። እነርሱ የእግዚአብሔር የቃል ኪዳን ሕዝብ መሆናቸው፣ ኢየሩሳሌምም ቤተ መቅደሱ ያለባት ከተማ መሆኗ፣ ከምርኮ ነጻ የሚሆኑበትን ጊዜ የሚያፋጥንና ኢየሩሳሌምም ከመደምሰስ እንደምትተርፍ የሚያረጋግጥ አይደለም (ኤር 29-30 ይመ)። ለነቢዩ አስረግጦ እንዲናገር የተሰጠው ተስፋ በምርኮ ጊዜ እርስ በርሳቸው እንዲሁም ከእግዚአብሔር ጋር በሰላም እንዲኖሩ ነው።

ኢየሩሳሌም እንደምትከበበና በእርግጥም እንደምትወድቅ (24፥1-14) ጌታ ከተናገረው በኋላ፣ ተወዳጅ ሚስቱም በቅርቡ እንደምትሞት ለሕዝቅኤል ተነግሮት ነበር። እስራኤል የዐይኗ አምሮት የሆነው ቤተ መቅደስ ከእርሷ እንደሚወሰድ ሁሉ፣ ሕዝቅኤልም የዐይኑ አምሮት የሆነችው ሚስቱ ከእርሱ ትወሰዳለች። ሕዝቡ ለኢየሩሳሌም በግልፅ እንዳያዝንና እንዳያለቅስ ምልክት ይሆን ዘንድ (24፥15-27)፣ ስለ ሚስቱ ሞት በግልጽ ማዘንና ማልቀስ አልነበረበትም። ከዚያም የእግዚአብሔርን ተከታታይ ፍርድ በሰባቱ አገሮች ማለትም በአሞን፣ በሞዓብ፣ በኤዶም፣ በፍልስጥኤም፣ በጢሮስ፣ በሲዶንና በግብፅ ላይ በቀጥታ እንዲናገር ታዝዞ ነበር (ም 25-32)። የእግዚአብሔር የቍጣ ቀን በእስራኤል ላይ ብቻ ሳይሆን በሌሎቹም ላይ በቅርቡ ይመጣል።

ስለ ኢየሩሳሌም መውደቅ አንድ ጊዜ ከተናገረ በኋላ፣ የሕዝቅኤል መልእክት እግዚአብሔር ለሕዝቡ ባለው የማጽናናትና የተስፋ ቃል ላይ ያተኰረ ነበር። ይህም የተስፋ ቃል እስራኤላውያን በዓለም ውስጥ የተዋጀና ፍጹም የእግዚአብሔር መንግሥት በመሆን፣ ተሐድሶን የሚለማመዱበትና ወደ ከበረ ሕይወት የሚመለሱበትን ጊዜ የሚያመለክት (ም33-48) ነው።

**መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ**

በብሉይ ኪዳን ከተጠቀሱት የትንቢት መጻሕፍት ይልቅ የሕዝቅኤል መጽሐፍ ብዙ የቀን መግለጫዎች የያዘ በመሆኑ፣ በውስጡ ያሉት ትንቢቶች ትክክለኛ ጊዜ ለይቶ ማመልከት ይቻላል። በተጨማሪም በዘመናዊ ዕውቀት፣ በባቢሎናውያን የኰኔፎርም ሰሌዳዎች ላይ ያለውን የዘመን አቈጣጠር በማንበብ የታሪካዊ ቅርሶች ጠቢባን ያገኙትን መረጃ እንዲሁም በጥንታዊ ሥነ ፅሑፎች ላይ የሚገኙትን የፀሓይና የጨረቃ ግርዶሽ የሆነበት ጊዜ በማጥናት ከዋክብት ተመራማሪዎች የደረሱበትን አቈጣጠር መሠረት በማድረግ ከአሁኑ የዘመን አቈጣጠር ጋር አንድ ዓይነትና እኩል የሆነ ትክክለኛ የዘመን አቈጣጠር ማመልከት ተችሏል።

ከዐሥራ ሦስቱ የቀን ማውጫዎች ወስጥ ዐሥራ ሁለቱ ሕዝቅኤል መለኮታዊውን መልእክት መቼ እንደተቀበለ ያሳያል። ሌላኛው ቀን የኢየሩሳሌምን መውደቅ የተናገረው መልእክተኛ የደረሰበትን ጊዜ የሚያመለክት ነው (33፥21)። ሐምሌ 593 ዓ.ቅ.ክ. ጥሪውን የተቀበለበት ጊዜ ሲሆን ሚያዝያ 571 ዓ.ቅ.ክ. ደግሞ የመጨረሻውን የትንቢት ቃል የተቀበለበት ጊዜ ነው፤ ስለዚህ ሕዝቅኤል ለሃያ ሁለት ዓመት አገልግሎአል ማለት ነው (29፥17 ይመ)። በ1፥1 ላይ የተጠቀሰው፣ "ሠላሳኛው ዓመት" ሕዝቅኤል ለአገልግሎት ሲጠራ የነበረውን ዕድሜ የሚያመለክት ከሆነ፣ በነቢይነት ያገለገለበት ጊዜ በደምቡ መሠረት የክህነት አገግሎት ከሚጀመርበት በሁለት ዓመት ያህል ይበልጣል ማለት ነው (ዘኍ 4፥3 ይመ)። የአገልግሎቱ ጊዜ የኢየሩሳሌም የጨለማ ዘመን ውስጥ ሲሆን፣ በ586 ዓ.ቅ.ክ ኢየሩሳሌም ከፈረሰ ችበት ሰባት ዓመት ቀደም ብሎ በመጀመር፣ ከዚያ በኋላ ለዐሥራ አምስት ዓመት ያህል ዘልቆአል።

**በሕዝቅኤል መጽሐፍ የተጠቀሱ ቀናት**

| | ጥቅሶች | ዓመት | ወር | ቀን | የዘመኑ አቈጣጠር በግምት | ድርጊት |
|---|---|---|---|---|---|---|
| 1 | 1፥1 | 30 | 4 | 5 | ዓ.ቅ.ክ. ሐምሌ 31/593 | የክብረ በዓል ራእይ |
| | 1፥2 | 5 | - | 5 | | |
| | 3፥16 | በሰባተኛው ቀን መጨረሻ | | | | |
| 2 | 8፥1 | 6 | 6 | 5 | ዓ.ቅ.ክ. መስከረም 17/592 | ወደ ኢየሩሳሌም ጉዞ |
| 3 | 20፥1-2 | 7 | 5 | 10 | ዓ.ቅ.ክ. ነሐሴ 14/591 | የእስራኤል ታሪክ አሉታዊ ገጽታ |
| 4 | 24፥1 | 9 | 10 | 10 | ዓ.ቅ.ክ. ጥር 15/588 | ከበባው የጀመረበት ጊዜ(2ነገ25፥1) |
| 5 | 26፥1 | 11 | - | 1 | ዓ.ቅ.ክ. ሚያዝያ 23/587 | |
| | | | | | እስከ ሚያዝያ 13/ 586 | በጢሮስ ላይ የተነገረ የትንቢት ቃል |
| 6 | 29፥1 | 10 | 10 | 12 | ዓ.ቅ.ክ. ጥር 7/587 | በግብፅ ላይ የተነገረ የትቢት ቃል |
| 7 | 29፥17 | 27 | 1 | 1 | ዓ.ቅ.ክ. ሚያዝያ 26/571 | ጢሮስን የተካችው ግብፅ |
| 8 | 30፥20 | 11 | 1 | 7 | ዓ.ቅ.ክ. ሚያዝያ 29/587 | በፈርዖን ላይ የተነገረ የትንቢት ቃል |
| 9 | 31፥1 | 11 | 3 | 1 | ዓ.ቅ.ክ. ሰኔ 21/587 | በፈርዖን ላይ የተነገረ የትንቢት ቃል |
| 10 | 32፥1 | 12 | 12 | 1 | ዓ.ቅ.ክ. መጋቢት 3/585 | ስለ ፈርዖን የተነገረ የልቅሶ እንጉርጉሮ |
| 11 | 32፥17 | 12 | - | 15 | ዓ.ቅ.ክ. ሚያዝያ 13/586 | |
| | | | | | እስከ ሚያዝያ 1/585 | የግብፅ ሞት |
| 12 | 33፥21 | 12 | 10 | 5 | ዓ.ቅ.ክ. ጥር 8/585 | የመጀመሪያዎቹ ስደተኞች የደረሱበት ጊዜ |
| 13 | 40፥1 | 25 , | 1 | 10 | ዓ.ቅ.ክ. ሚያዝያ 28/573 | ስለወደፊቱ የተጠቀሰው ራእይ |
| | 40፥1 | "ከከተማዪቱ መውደቅ ዐሥራ አራት አመት በኋላ" | | | | |

**መሪ ሐሳብ**

ብሉይ ኪዳን በአጠቃላይ በተለይም የነቢያት መጻሕፍት እግዚአብሔር ከፍጥረት ሁሉ በላይ፣ ከሕዝብና ከመንግሥታት እንዲሁም ከታሪክ ሂደት ሁሉ በላይ መሆኑን ያስተምራሉ:: እግዚአብሔር ታሪክ እንዲፈጠር የሚያደርግና ሂደቱንም የሚቈጣጠር መሆኑ ግልፅና ቀጥተኛ በሆነ መንገድ የተገለጸበት ክፍል ከመጽሐፍ ቅዱስ እንደ ሕዝቅኤል መጽሐፍ ያለ የለም:: የእግዚአብሔር መለኮታዊ መገኘት ስዕላዊ በሆነ መንገድ ከተገለጸበት ከመጀመሪያው ምዕራፍ አንሥቶ የሕዝቅኤልን ራእይ እስከሚገልጸው የመጨረሻው ሐረግ ድረስ መጽሐፉ የእግዚአብሔርን ሉዓላዊነት ይገልጻል::

ይህ ሉዓላዊ አምላክ ሰዎች እንዲያውቁትና እንዲያከብሩት አድርጎአል:: በዚህ መጽሐፍ ውስጥ፣ "እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ" የሚለው ሐረግ በብዛት ተደጋግሞ መጻፉ፣ እግዚአብሔር ሰዎች እንዲያውቁት አጥብቆ የሚፈልገው ጉዳይ እንደ ሆነ ይመሰክራል:: እግዚአብሔር በኢየሩሳሌም መውደቅና በቤተ መቅደሱ መፍረስ ራሱን እንደሚገልጽ ከም1-24 የተጠቀሰው ትምህርት ያመለክታል:: እንዲሁም ከም25-32 ያለው ክፍል መንግሥታትና ሕዝቦቻቸው እግዚአብሔርን በፍርዱ እንደሚያውቁት ይገልጻል:: በተጨማሪም ከምዕራፍ 33-48 በተሰጠው የተስፋ ቃል እግዚአብሔር የእስራኤልን መንግሥት በመመለሱና መንፈሳዊ ተሐድሶን በማምጣቱ እንደሚታወቅ ተገልጾአል::

የእግዚአብሔር ሉዓላዊነት በአንድ ስፍራ የተወሰነ ባለመሆኑም ተገልጾአል:: ኢየሩሳሌም ባለው ቤተ መቅደስ አልተወሰነም:: በእስራኤል ያለውን ቤተ መቅደስ በመተው፣ ሕዝቡ ባሉበት በሚሠሩትም ኀጢአት ሊቀጣቸው ይችላል፤ ደግሞም ወደ ባቢሎን ተማርከው በሄዱትም ሕዝብ መካከል ተገኝቶ በምሕረቱ እንደሚጐበኛቸውም ተጠቅሶአል::

እግዚአብሔር ለመፍረድም ሆነ ምሕረት ለማድረግ ነጻ ነው፤ እግዚአብሔር በእስራኤል ላይ የወሰነው ከባድ ፍርድ በመጨረሻ የጸጋውን ታላቅነት ያሳያል:: የሕይወቷ መታደስና የእርሱም ከእርሷ ጋር መሆን የፍጥረተ ዓለም ጌታ የሆነው የእግዚአብሔር ስጦታ እንደ ሆነ በግልፅ ይታወቅ ዘንድ፣ እግዚአብሔር የእስራኤል ፖለቲካዊ ማንነትና መንፈሳዊ ሕይወት ደብዛው እንዲጠፋ ያደርጋል::

ከዚህም በላይ፣ ሕዝቅኤል አፈ እግዚአብሔር እንደመሆኑ፣ "የሰው ልጅ" በማለት የጠቀሰው ማዕረግ የሚያመለክተው ቃል፣ (የ2፥1 ማብ ይመ)፣ ሊያገለግል የተላከውን ልዑል እግዚአብሔር ሁኔታ ይመሰክራል::

**ሥነ ጽሑፋዊ ይዘት**

ሶፎንያስና ሦስቱ ዋና ነቢያት ማለት ኢሳይያስ፣ ኤርምያስና ሕዝቅኤል ሁሉም ተመሳሳይ የሆነ መሠረታዊ የመልእክት አቀራረብ ሂደት አላቸው፤ (1) በእስራኤል ላይ የተነገረ የትንቢት ቃል (2) በአሕዛብ መንግሥታት ላይ የተነገረ የትንቢት ቃል (3) ስለ እስራኤል የተነገረ የማጽናኛ ቃል:: ይህ ሂደት ከሌሎቹ መጻሕፍት ይልቅ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ላይ ግልፅ ሆኖ ተቀምጦአል::

ከሥነ ጽሑፋዊ አወቃቀሩ ግልጽነት ባሻገር፣ የሕዝቅኤል መጽሐፍ የእኵዮሽ አቀራረብ ይታይበታል:: በመርከሱ መጥፋት ስለሚገባው ቤተ መቅደስ የታየው ራእይ (ም 8-11) የነጻውንና እንደ ገና የታነጸውን ቤተ መቅደስ በሚመለከት ከታየው ራእይ ጋር (ም 40-48) እኵያ ነው:: በአስደንጋጭ ቍጣው (ም 1) የተገለጸው እግዚአብሔር፣ አጽናኝ አምላክ መሆኑም ተገልጾአል ("እግዚአብሔር በዚያ ነው" 48፥35 የሚለውን ይመ):: መለኮታዊው ፍርድ ጠባቂ ለመሆን ሕዝቅኤል የተጠራበት ጥሪ (ም 3) በአዲሱ ዘመን ጕበኛ ለመሆን ከተጠራበት ጥሪ ጋር (ም 33) ሚዛናዊ ሆኖአል:: በም6 የእስራኤል ተራሮች ትንቢታዊ ግሣጼን ሲቀበሉ፣ በም 36ግን የሚያጽናና ቃል ተሰጥቶአቸዋል::

የነቢያት መጽሐፍ በአብዛኛው ቅኔአዊ ሲሆኑ፣ ነቢያት መልእክታቸውን ያስተላለፉት በግጥምና በዜማ ነው:: አብዛኛው የሕዝቅኤል ትንቢት አቀራረብ ስድ ንባብ የሆነው፣ ምናልባትም ከካህናት ወገን ስለሆነ ይሆናል:: ሐሳብን ደጋግሞ የማቅረብ ሥልቱ፣ ትኵረት እንዲሰጠው የተፈለገውን ነገር ለማስጨበጥ የሚያስችል ነው:: በመልእክቶቹ ላይ የተጠቀሱት የሕግና የሥርዐት ይዘት ያላቸው ሐሳቦች፣ የሕዝቅኤልን የክህነት ዕውቀት የሚያንጸባርቍ ናቸው (3፥19 ከዘፀ 21፥2 ጋር ያነጻጽሩ)::

የሕዝቅኤል መጽሐፍ አራት ራእዮችን (ም 1-3፤ 8-11፤ 37፥1-14፤ 40-48) እንዲሁም ዐሥራ ሁለት ትእምርታዊ ድርጊቶችን (3፥22-26፤ 4፥1-3፤ 4፥4-8፤ 4፥9-11፤ 4፥12-14፤ 5፥1-3፤ 12፥1-16፤ 12፥17-20፤ 21፥6-7፤ 21፥18-24፤ 24፥15-24፤ 37፥15-28) የያዘ ሲሆን፣ አምስት መልእክቶች ደግሞ በምሳሌ ቀርበዋል (ም 15፤ 16፤ 17፤ 19፤ 23)::

**ትምህርተ መለኮታዊ ገጽታ**

ሌሎች ነቢያት እስራኤል ጣዖት ማምለኳን፣ በአደባባይም ሆነ በጓዳ በምታደርጋቸው ጉዳዮች ሥነ ምግባራዊ ጕድለቷን፣ በእግዚአብሔር ከመታመን ይልቅ በሌሎች መንግሥታት በመደገፍ ያደረገችውን ትብብርና ዐመፅ ተናግረዋል:: እግዚአብሔር ባመፀኛ ሕዝቡ ላይ የወሰነውን ሊፈጽም ያለውን ፍርድ ቢያሳውቅም፣ ስለሚመጣው የመታደስ ዘመንን በማስመልከት ስለ እስራኤል ከየአገሩ መመለስ፣ አዲስ ኪዳን፣ የታደሰችው ኢየሩሳሌም፣ የታደሰው የዳዊት ስርወ መንግሥት፣ የክርስቶስ ጌትነትና መሲሕነት በዓለም ሁሉ መታወቅና ስለሚኖረው ፍጹም ሰላም ይናገራል::

በትንቢተ ሕዝቅኤል ውስጥ ያለው የመልእክት ዝርዝር ማውጫና ሐተታ ተመሳሳይ ነው፤ ይሁን እንጂ ሕዝቅኤል በመልእክቱ በአፅንኦት የሚገልፀው እስራኤል የተቀደሰው ቤተ መቅደስ፣ የቅድስቲቱ

ከተማና የቅድስቲቱ ምድር ቅዱስ ሕዝብ እንደ ሆነ ነው:: እስራኤል አምልኮዋን በማበላሸት ራስዋን አረከሰች፤ እንዲሁም ቤተ መቅደሱን፣ ከተማውንና ምድሪቱን አርክሳለች:: ከዚህ ርኵሰት የተነሣም እግዚአብሔር ራሱን ከእስራኤል ያርቃል፤ ጥፋትንም በማምጣት በሕዝቡ ላይ ይፈርዳል::

ነገር ግን እግዚአብሔር ኪዳኑን ለማክበር ያለው ታማኝነትና ለማዳን ያለው ፍላጐት እጅግ ታላቅ ከመሆኑ የተነሣ እንደገና አንድ ጊዜ ለመጨረሻ ሕዝቡን ያነቃቃል፤ በርኅራኄ ይመራቸዋል፤ ከርኵሰታቸው ሁሉ ያነጻቸዋል፤ በተስፋዪቱ ምድር የእርሱ መንግሥት ፍጹም ምሳሌ ሆነው እንዲቆሙ፣ በዳዊት እጅ እንደገና ይመሠርታቸዋል:: የዳዊትም መንግሥት በዙሪያው የተነሡትን ጠላቶች በማሸነፍ፣ የእግዚአብሔርን ክብር በአሕዛብ መካከል ገለጠ፤ በቅድስቲቱም ከተማ እግዚአብሔር መኖሩን አሳወቀ::

ነቢዩ ሕዝቅኤል ኀይል በተሞላ አነጋገር የእግዚአብሔርን ታላቅነትና ክብር የተሞላውን አገዛዙን እንዲሁም በቅንዓት የሚጠብቀውን ቅድስና ገለጠ:: የመጽሐፉ ሥነ መለኮታዊ ዋና ሐሳብ፣ እግዚአብሔር በዓለም ታሪክ ውስጥ የገለጠውን ሰውን የማዳኑን ዐላማ የሚያመለክት ነው:: ይህም የቃል ኪዳን ሕዝቡ በመርከሱ እግዚአብሔር ከእነርሱ ፈቀቅ ካለበት ጊዜ ጀምሮ ሕዝቡን ለማዳን ያቀደበት ጊዜ እስከሚደርስበት ያለውን ማለት ነው:: የሕዝቅኤል መልእክት በከፍተኛ ደረጃ በነገረ ፍጻሜ በሚከናወነው ላይ የሚያተኵር ሲሆን፣ በአዲስ ኪዳን የተገለጸውን ወደፊት እግዚአብሔር በታሪክ ውስጥ የሚሠራውን ያሳያል::

**አስተዋፅዖ**

1 በእስራኤል ላይ የተነገረ የፍርድ ቃል (ንግር) (ም 1-24)
- ሀ. የሕዝቅኤል የመክፈቻ ራእይ (ም 1-3)
  1. የመለኮታዊ ክብር መገለጥ (ም 1)
  2. መታጠቅና መልእክተኛ መሆን (2፥1-3፥15)
  3. ጕበኛው (3፥16-21)
  4. ለተጨማሪ ማሳሰቢያዎች (3፥22-27)
- ለ. የኢየሩሳሌምን መከበብ የሚያመለክቱ ትእምርታዊ ድርጊቶች (ም 4-5)
  1. የኢየሩሳሌም ከተማ በሸክላ ሠሌዳ ላይ (4፥1-3)
  2. በነቢዩ አለመንቀሳቀስ የኢየሩሳሌም ከበባ መገለፁ (4፥4-8)
  3. በምርኮውና በከበባው ጊዜ የሚበላው ምግብ (4፥9-17)
  4. አስደናቂው መላጪያና ሥራው (ም 5)
- ሐ. መለኮታዊውን ፍርድ የሚገልጡ ንግሮች (ም 6-7)
  1. የእስራኤል ተራሮች መውደም (ም 6)
  2. የፍጻሜው መምጣት (ም 7)
- መ. ስለረከሰው ቤተ መቅደስ የታየው ራእይ (ም 8-11)
  1. አራት አስጸያፊ ነገሮች (ም 8)
  2. የከተማዪቱ መደምሰስ (ም 9)
  3. የእግዚአብሔር ክብር ኢየሩሳሌምን ትቶ መሄዱ (ም 10)
  4. የራእዩ ማጠቃለያ (ም 11)
- ሠ. የኢየሩሳሌምን መማረክ የሚያመለክቱ ትእምርታዊ ድርጊቶች (ም 12)
  1. የስደተኛ ጓዝ (12፥1-16)
  2. የችኰላ መብል (12፥17-20)
  3. የፍርድ ቀን መቅረቡ (12፥21-28)
- ረ. መለኮታዊ ፍርድ የሚገልጡ ንግሮች (ም 13-24)
  1. ሐሰተኛ ነቢያትና የአስማት ሥራቸው (ም 13)
  2. በጣዖት አምልኮ ላይ የሚገለጥ ፍርድ (14፥1-11)
  3. ኖኅ፣ ዳንኤልና ኢዮብ (14፥12-23)
  4. ኢየሩሳሌም እንደ ተቃጠለ የወይን ቅርንጫፍ (ም 15)
  5. ኢየሩሳሌም ከወላጅ ጠፍታ እንደተገኘች ሕፃን (16፥1-43)
  6. ኢየሩሳሌም ከሌሎች ከተሞች ጋር ስትነጻጸር (16፥44-63)
  7. የኢየሩሳሌም ነገሥታት በምሳሌ ሲገለጹ (17፥1-21)
  8. አዲሱ ዛፍ (17፥22-24)
  9. ከሦስት ትውልድ የተገኘ ትምህርት (ም 18)
  10. ሁለት ገጽታ ያለው ሙሾ (ም 19)
  11. እስራኤል በልበ ድንዳኔ ደጋግማ ኀጢአት መሥራቷ (ም 20)
  12. የእግዚአብሔር ሰይፍ (ም 21)
  13. ኢየሩሳሌም የደም ከተማ (ም 22)
  14. ኦሖላና ኦሖሊባ (ም 23)

15. የፍጻሜው እሳት፣ የኢየሩሳሌም መጨረሻ (24፥1-14)
16. የሕዝቅኤል ሚስት መሞትና የቤተ መቅደሱ መደምሰስ (24፥15-27)

2 በአሕዛብ መንግሥታት ላይ የተነገረ የፍርድ ንግር (ም 25-32)
ሀ. በአሞን ላይ (25፥1-7)
ለ. በሞዓብ ላይ (25፥8-11)
ሐ. በኤዶም ላይ (25፥12-14)
መ. በፍልስጥኤም ላይ (25፥15-17)
ሠ. በጢሮስ ላይ (26፥1-28፥19)
1. የከተማይቱ መጨረሻ (ም 26)
2. ለጢሮስ የተደረገ ሙሾ (ም 27)
3. በጢሮስ ንጉሥ ላይ የተነገረ (28፥1-19)
ረ. በሲዶና ላይ የተነገረ (28፥20-24)
ሰ. ለእስራኤል የተነገረ የተስፋ ማስታወሻ (28፥25-26)
ሸ. በግብፅ ላይ የተነገረ (ም 29-32)
1. የተጣለ አውሬ ስለ መሆኑ (29፥1-16)
2. ለናቡከደነፆር የተከፈለ ደመወዝ ስለመሆኑ (29፥17-21)
3. በመምጣት ላይ ያለው ቀን (30፥1-19)
4. የፈርዖን ክንድ መሰበር (30፥20-26)
5. ፈርዖን የወደቀ ዝግባ ስለመሆኑ (ም 31)
6. ለፈርዖን የተደረገ ሙሾ (32፥1-16)
7. ካልተገረዙት ጋር ወደ ጉድጓድ ስለመጣሉ (32፥17-32)

3 ስለ እስራኤል መጽናናት የቀረበ ንግር (ም 33-48)
ሀ. ጉብኛው (33፥1-20)
ለ. የኢየሩሳሌም መውደቅ መነገሩና መገለጡ (33፥21-33)
ሐ. እግዚአብሔር እንደ መልካም እረኛ መገለጡ (ም 34)
መ. በኤዶም ላይ የቀረበ ንግር (ም 35)
ሠ. የእስራኤልን ተራሮች የሚያጽናና ቃል (36፥1-15)
ረ. የትንቢተ ሕዝቅኤል ነገረ መለኮት ማጠቃለያ (36፥16-38)
ሰ. ስለ ሕዝቡና ስለ አገሪቱ እንደ ገና መታደስ የታየ ራእይ (ም 37)
1. ብሔራዊ ትንሣኤ (37፥1-14)
2. የእስራኤልና የይሁዳ ተመልሶ መዋሃድ (37፥15-28)
ሸ. የመጨረሻው ጦርነት (ም 38-39)
ቀ. በተሐድሶ ስለሚደረገው አምልኮ የታየ ራእይ (ምዕ 40-48)
1. በቤተ መቅደሱ ዙሪያ ያለው ቅጥር (40፥1-47)
2. የቤተ መቅደሱ የውጪ አደባባይ (40፥48-41፥26)
3. የቤተ መቅደሱ የውስጥ አደባባይ (ም 42)
4. የእግዚአብሔር ክብር መመለስ (ም 43)
5. የክህነት አገልግሎት (ም 44)
6. የመሬት ድልድል (ም 45)
7. የአለቃው ተግባር (ም 46)
8. ሕይወት የሚሰጠው ውሃ (47፥1-12)
9. የመሬት ድልድል (47፥13-48፥35)

## ሕያዋኑ ፍጡራንና የእግዚአብሔር ክብር

**1** በሠላሳኛው ዓመት፣[ሀ] በአራተኛው ወር፣ በአምስተኛው ቀን፣ በኮቦር ወንዝ አጠገብ በምርኮኞች መካከል ሳለሁ፣ ሰማያት ተከፈቱ፤ እኔም የእግዚአብሔርን ራእይ አየሁ::

[2]ንጉሡ ዮአኪን በተማረከ በአምስተኛው ዓመት፣ በአምስተኛው ቀን፣ [3]በባቢሎናውያን[ለ] ምድር በኮቦር ወንዝ አጠገብ፣ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ ቡዝ ልጅ፣[ሐ] ወደ ካህኑ ወደ ሕዝቅኤል መጣ፤ በዚያ *የእግዚአብሔር* እጅ በእርሱ ላይ ነበረች::

[4]እኔም አየሁ፤ ስመለከትም፣ እነሆ ዐውሎ ነፋስ ከሰሜን በኩል መጣ፤ ይኸውም ቢታላቅ ብርሃን የተከበበ፣ መብረቅን የሚረጭ ታላቅ ደመና ነበረ፤ የእሳቱም መኻል የጋለ ብረት ይመስል ነበር:: [5]በእሳቱም ውስጥ የአራት ሕያዋን ፍጡራን አምሳያ ነበረ፤ መልካቸውም የሰው ቅርጽ ይመስል ነበር:: [6]እያንዳንዳቸውም አራት አራት ፊትና አራት አራት ክንፍ ነበራቸው:: [7]እግራቸው ቀጥ ያለ ነበር፤ ኮቴያቸውም እንደ ጥጃ ኮቴ ያለ ሲሆን፣ እንደ ተወለወለ ናስም ያብለጨልጭ ነበር:: [8]በአራቱ ጐኖቻቸው ባሉት ክንፎቻቸው ሥር የሰው እጅ ነበራቸው:: አራቱም ፊቶችና ክንፎች ነበሯቸው፤ [9]ክንፎቻቸውም እርስ በርስ ይነካኩ ነበር:: እያንዳንዱም ቀጥ ብሎ ይሄድ ነበር፤ ወደ ኋላቸውም ዞር ብለው አይመለከቱም ነበር::

[10]ፊታቸውም እንዲህ ነበር፤ አራቱም እያንዳንዳቸው የሰው ፊት ነበራቸው፤ በቀኝ በኩል የአንበሳ ፊት፣ በግራ በኩልም የበሬ ፊት ነበራቸው፤ እያንዳንዳቸውም ደግሞ የንስር ፊት ነበራቸው:: [11]እንግዲህ ፊታቸው ይህን ይመስል ነበር፤ ክንፋቸውም ወደ ላይ ተዘርግቶ ነበር፤ እያንዳንዳቸው ሁለት ሁለት ክንፍ ነበራቸው፤ የእያንዳንዱም ክንፍ የሌላውን ክንፍ ይነካ ነበር፤ ሁለቱ ክንፎቻቸው ሰውነታቸውን ይሸፍኑ ነበር:: [12]እያንዳንዱ ቀጥ ብሎ ወደ ፊት ይሄድ ነበር፤ ወደ ኋላም ሳይዞር መንፈስ ወደሚሄድበት ሁሉ ይሄድ ነበር:: [13]የሕያዋን ፍጡራኑ መልክም እንደሚነድ የከሰል ፍምና የተቀጣጠለ ችቦ ይመስል ነበር፤ በፍጡራኑ መካከል እሳት ወዲያ ወዲህ ይንቀሳቀስ ነበር፤ ብርሃኑም ደማቅ ነበር፤ ከእሳቱም ውስጥ መብረቅ ይወጣ ነበር:: [14]ፍጡራኑም እንደ መብረቅ ብልጭታ ፍጥነት ወዲያ ወዲህ ይወረወሩ ነበር::

[15]ሕያዋን ፍጡራኑን ስመለከታቸው፣ አራት ፊቶች ባሉት በእያንዳንዱ ፍጡር አጠገብ አንዳንድ መንኰራኵር በምድር ላይ አየሁ:: [16]የመንኰራኵሮቹ መልክና አሠራር እንዲህ ነበር፤ እንደ ቢረሌ ያንጸባርቁ ነበር፤ የአራቱም ቅርጽ ተመሳሳይ ሆኖ፤ እያንዳንዱ መንኰራኵር በመንኰራኵር ውስጥ ተሰክቶ የተሠራ ይመስል ነበር:: [17]በሚሄዱበት ጊዜም፣ ፍጡራኑ ወደሚዞሩበት ወደ አራቱ አቅጣጫ ሁሉ መንቀሳቀስ ይችሉ ነበር፤ ፍጡራኑ በሚሄዱበትም ጊዜ መንኰራኵሮቹ ወዲያና ወዲህ[መ] አይሉም ነበር:: [18]የመንኰ

[ሀ]1 ወይም *ዓመቴ*
[ለ]3 ወይም *በከለዳውያን*
[ሐ]3 ወይም *ወደ ካህኑ ቡዝ ልጅ ወደ ሕዝቅኤል*
[መ]17 ወይም *ወደ ሌላ*

1፥1 ዘፀ24፥10፤ዘዳ 21፥10፤መዝ137፥1፤ ሕዝ11፥24-25፤ ማቴ3፥16
1፥2 2ነገ24፥15
1፥3 2ነገ3፥15፤ኢሳ 8፥11፤ሕዝ3፥14፡22፤ 8፥1፤24፥24፤33፥22፤ 37፥1፤40፥1
1፥4 ኢዮ38፥1፤ኤር 1፥14፤ሕዝ8፥2
1፥5 ቍ26፤ኢሳ6፥ 2፤ዳን7፥13፤ራእ4፥6
1፥6 ሕዝ10፥14
1፥7 ሕዝ40፥3፤ ዳን10፥6፤ራእ1፥15
1፥8 ሕዝ10፥8
1፥9 ሕዝ10፥22
1፥10 ሕዝ10፥14፤ ራእ 4፥7
1፥11 ኢሳ6፥2
1፥12ሕዝ10፥16-19
1፥13 2ሳሙ22፥9፤ ራእ4፥5
1፥14 መዝ29፥7
1፥15 ሕዝ3፥13፤ 10፥2፤ዳን7፥9
1፥16 ዘፀ28፥20
1፥17 ቍ9
1፥18 ራእ4፥6

1፥1 *በሠላሳኛው ዓመት፤* ምናልባት ይህ አኀዝ የሕዝቅኤልን ዕድሜ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (አማራጭ ትርጕሙን ይመ):: በዘኍ4፥3 መሠረት፣ አንድ ሰው በሌዋውያን ሥርዐተ ክህነት፣ አገልግሎት የሚጀምረው ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ሲሞላ ነው:: ሕዝቅኤል በምርኮ ላይ በነበረበት ጊዜ በክህነት አገልግሎት መቀጠል ባይችልም፣ ለነቢይነት አገልግሎት ግን ተጠራ:: *ኮቦር ወንዝ፤* ከባቢሎን በስተ ደቡብ፣ ከኒፑር ከተማ አጠገብ ያለ የኤፍራጥስ ወንዝ የመስኖ ቦይ ነው፤ ምናልባትም ቦታው የምርኮኞች የጸሎት ስፍራ ሳይሆን አይቀርም (መዝ 137፥1 ይመ፤ ከሐሥ16፥13 ጋር ያነጻጽሩ):: *የእግዚአብሔርን ራእይ፤* ይህ ሐረግ ለየት ያለ አገባብ ያለው ሲሆን፣ ነቢዩ ካያቸው ሁለት ዋና ራእዮች ቀደምትነት አለው (8፥3፤ 40፥2 ይመ)::

1፥2 *ንጉሡ ዮአኪን፤* በዓ.ቅ.ክ. 597 የመጀመሪያዎቹን ምርኮኞች ይዞ ወደ ባቢሎን ገባ፤ ሕዝቅኤልም ከእነዚህ ምርኮኞች አንዱ ሲሆን፣ ለነቢይነት አገልግሎት የተጠራውም በ593 ዓ.ቅ.ክ. ነው:: *በተማረከ በአምስተኛው ዓመት፤* ከቍ2-3 ያለው ሐሳብ በሦስተኛ መደብ መቅረቡ በቍ1 ላይ የተጠቀሰውን ዘመን ግልጽ ያደርገዋል::

1፥3 *ሕዝቅኤል፤* 24፥24 ይመ፤ የስሙ ትርጕም፣ "እግዚአብሔር ብርቱ ነው" (ከ3፥14 ጋር ያነጻጽሩ)፣ "እግዚአብሔር ያበረታል" (ከ30፥25፤ 34፥16 ጋር ያነጻጽሩ) ወይም "እግዚአብሔር ጠንካራ ያደርጋል" (ከ3፥8 ጋር ያነጻጽሩ) ማለት ነው:: በ1ዜና24፥16 ላይ የተጠቀሰው፣ "ኢዚኤል" የሚለው ስምና "ሕዝቅኤል" የሚለው ስም በዕብራይስጥ ትርጕሙ አንድ ነው:: ሆኖም ግን እነዚህ ሰዎች አንድ አይደሉም:: *ካህኑ፤* ከካህናት ቤተ ሰብ መሆኑን የሚያመለክት ነው (አማራጭ ትርጕሙን ይመ):: *የእግዚአብሔር እጅ፤* ይህ ሐረግ በመጽሐፉ ውስጥ ስድስት ጊዜ በተከታታይ ተጠቅሶአል (3፥14፡22፤ 8፥1፤ 33፥22፤ 37፥1፤ 40፥1):: ይህም የተገለጠለት ራእይ በመለኮታዊ ኀይል መሆኑን ያመለክታል::

1፥4 *ስመለከትም፤* ይህ የራእዩን የመጀመሪያ ክፍል ያመለክታል፤ የተመለከታቸውም ነፋስና ሕያዋን ፍጡራን ናቸው (ቍ4-14):: በቍ15 ላይ፣ "ስመለከታቸው" የሚለው ቃል፣ የራእዩ ሁለተኛ ክፍል መግቢያ ነው፣ እዚህ ላይ የሚያመለክተው ደግሞ መንኰራኵሮቹንና የእግዚአብሔርን ክብር ነው:: *ዐውሎ ነፋስ፤* መዝ18፥10-12 ይመ::

1፥5 *አራቱ ሕያዋን ፍጡራን፤* "አራት" የሚለው ቃል የሚያመለክተው ሙሉነትን፣ ፍጹምነትን ነው (በዘፍ13፥14 ላይ ከተጠቀሰው፣ "አራት አቅጣጫዎች" ከሚለውና በኢሳ11፥12 ላይ ከተጠቀሰው "አራቱ የምድር ማዕዘናት" ጋር ያነጻጽሩ) ይህ ቃል በዚህ ምዕራፍ ላይ በተደጋጋሚ የተጠቀሰ ሲሆን፣ በዚህ መጽሐፍ ደግሞ ከአርባ ጊዜ በላይ ተጠቅሶ ይገኛል:: በም10 ላይ "ኪሩቤል" የተባሉት፣ እነዚህ ሕያዋን ፍጡራን በዙፋኑ ዙሪያ የሚገኙ ሲሆኑ፣ በዚህ ስፍራ ላይ (ቍ10) የእግዚአብሔርን ፍጥረታት ይወክላሉ፤ "ሰው"፣ በእግዚአብሔር ፍጥረታት ላይ ገዥ (ዘፍ 1፥26-28፤ መዝ8 ይመ)፤ "አንበሳ"፣ ከዱር አራዊት ሁሉ ኀያል፣ "በሬ"፣ ከቤት እንስሳት ሁሉ እጅግ ብርቱ ሲሆን፣ "ንስር" ደግሞ ከአዕዋፍ ሁሉ ኀይለኛ ነው:: እነዚህ አራቱ ፍጡራን በራእ 4፥7 ላይም ተጠቅሰዋል፤ በመካከለኛው ዘመን በነበሩት ሥዕሎችና ቅርጾች፣ አራቱን ወንጌላት እንደሚወክሉ ተገልጾአል::

1፥7 *እንደ ጥጃ፤* ምናልባት ቀልጣፋነትን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ከመዝ29፥6፤ ሚል4፥2 ጋር ያነጻጽሩ)::

1፥12 *መንፈስ፤* ቍ20 ይመ::

1፥16 *ቢረሌ፤* መልኩ ምን እንደሚመስል መግለጽ አይቻልም፤ በዘፀ28፥20 (አማራጭ ትርጕሙን ይመ) ላይ የተገለጸውን በካህኑ ደረት ላይ የሚደረገውን የከበረ ድንጋይ ይመ:: *የእያንዳንዱ መንኰራኵር በመንኰራኵር ውስጥ ተሰክቶ፤* ምናልባት ሁለት መንኰራኵሮች በአራቱም አቅጣጫ ሊንቀሳቀሱ በሚችሉበት ሁኔታ በአራት ማእዘናት የተገጣጠሙ ይመስላል (ቍ17 ይመ):: ምስሉ፣ የእግዚአብሔርን በሁሉም ቦታ መገኘት ያመለክታል::

ራኰሮቹ ክብ ጠርዝ ረጅምና አስፈሪ ነበር፤ የአራቱም መንኰራኵሮች ክብ ጠርዝ ዙሪያውን በዐይኖች የተሞላ ነበር፡፡

[19]ሕያዋኑ ፍጡራን ሲንቀሳቀሱ፣ በአጠገባቸው ያሉ መንኰራኵሮችም ይንቀሳቀሱ ነበር፤ ሕያዋኑ ፍጡራን ከምድር ከፍ ከፍ ሲሉ፣ መንኰራኵሮቹም አብረዋቸው ከፍ ከፍ ይሉ ነበር፡፡ [20]መንፈስ ወደሚሄድበት ሁሉ ይሄዳሉ፤ የሕያዋኑ ፍጡራን መንፈስ በውስጣቸው ስላለ መንኰራኵሮቹ አብረዋቸው ይነሣሉ፤ [21]ፍጡራኑ ሲንቀሳቀሱ ይንቀሳቀሳሉ፤ ፍጡራኑ ቀጥ ብለው ሲቆሙ እነርሱም ይቆማሉ፤ ፍጡራኑ ከምድር ከፍ ከፍ ሲሉ፣ የሕያዋኑ ፍጡራን መንፈስ በውስጣቸው ስላለ መንኰራኵሮቹ አብረዋቸው ይነሣሉ፡፡

[22]ከሕያዋኑ ፍጡራን ራስ በላይ የሚያስፈራና፤ እንደ በረዶ የሚያንጸባርቅ ጠፈር የሚመስል ነገር ነበር፡፡ [23]ከጠፈሩም በታች የአንዱ ክንፍ ወደ ሌላው ተዘርግቶ ነበር፤ እያንዳንዱም ሰውነቱን የሚሸፍንበት ሁለት ክንፍ ነበረው፡፡ [24]ፍጡራኑ በሚንቀሳቀሱበት ጊዜ የክንፎቻቸውን ድምፅ ሰማሁ፤ ድምፁም እንደሚጐርፍ ውሃ ጩኸት፣ ሁሉን እንደሚችል" አምላክ ድምፅና እንደ ሰራዊት ውካታ ነበር፡፡ መንቀሳቀሳቸውን ሲያቆሙም ክንፎቻቸውን ዝቅ ያደርጉ ነበር፡፡

[25]መንቀሳቀሳቸውን አቁመው ክንፎቻቸውን ዝቅ እንዳደረጉ፣ ከራሳቸው በላይ ካለው ጠፈር ድምፅ ተሰማ፡፡ [26]ከራሳቸው በላይ ካለው ጠፈር ከፍ ብሎ የሰንፔር‘ ዙፋን የሚመስል ነገር ነበር፤ በዙፋኑም ላይ የሰው መልክ የሚመስል ነበር፡፡ [27]ወገቡ ከሚመስለው ጀምሮ ወደ ላይ በእሳት መካከል እንዳለ የጋለ ብረት፣ ከወገቡም በታች እሳት ይመስል እንደነበር አየሁ፤ ደማቅ ብርሃንም በዙሪያው ነበር፡፡ [28]በዝናብ ቀን በደመና ውስጥ እንደሚታየው ቀስተ ደመና በዙሪያው ያለው ጸዳል እንዲሁ ነበር፡፡

ይህም *የእግዚአብሔር* ክብር መልክ አምሳያ ነበረ፡፡ ባየሁትም ጊዜ በግንባሬ ተደፋሁ፤ የአንድ ተናጋሪን ድምፅ ሰማሁ፡፡

**የሕዝቅኤል መጠራት**

**2** እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ተነሥተህ በእግርህ ቁም፤ እኔም እናገርሃለሁ" አለኝ፡፡ [2]እርሱም ሲናገር፣ መንፈስ ወደ ውስጤ ገብቶ በእግሬ አቆመኝ፤ ሲናገረኝም ሰማሁት፡፡

[3]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ በእኔ ላይ ወደ ዐመፀው ወደ ዐመፀኛው የእስራኤል ሕዝብ እልክሃለሁ፤ እነርሱና አባቶቻቸው እስከ ዛሬ ድረስ ዐምፀውብኛል፡፡ [4]ሕዝቡም እልኸኛና ዐንገተ ደንዳና ነው፤ እኔ ወደ እነርሱ እልክሃለሁ፤ አንተም 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል' በላቸው፡፡ [5]እነርሱ ዐመፀኛ ቤት ስለ ሆኑ፤ ቢሰሙም ባይሰሙም በመካከላቸው ነቢይ እንደነበር ያውቃሉ፡፡ [6]አንተ የሰው ልጅ ሆይ፤ እነርሱን ወይም ቃላቸውን አትፍራ፤ ኵርንችትና እሾኽ በዙሪያህ ቢኖሩም፣ በጊንጦች መካከል ብትቀመጥም አትፍራ፡፡ እነርሱ ዐመፀኛ ቤት ቢሆኑም፣ አንተ በሚሉህ ነገር አትፍራ፤ እነርሱም አያስደንግጡህ፡፡ [7]እነርሱ ዐመፀኛ ቤት ስለሆኑ፣ ቢሰሙም ባይሰሙም አንተ ቃሌን ንገራቸው፡፡ [8]አንተ ግን የሰው ልጅ ሆይ፤ እኔ የምልህን ስማ፤ እንደዚያ ዐመፀኛ ቤት ዐታምፅ፤ አፍህን ክፈት፤ የምሰጥህንም ብላ፡፡"

[9]ከዚህም በኋላ፣ እነሆ አንድ እጅ ወደ እኔ ተዘርግቶ አየሁ፤ ጥቅልል መጽሐፍም ነበረበት፤ [10]እርሱም በፊቴ ዘረጋው፤ መጽሐፉም ከፊትና ከኋላው የሰቈቃ፣ የልቅሶና የዋይታ ቃላት ተጽፎበት ነበር፡፡

**3** እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ በፊትህ ያለውን ብላ፤ ይህን ጥቅልል መጽሐፍ

"24 በዕብራይስጡ *ሻዳይ ይላል*
‘26 ወይም *ላፒስ ላዙሊ*

1፥20 ቍ12
1፥21 ሕዝ10፥9-12
1፥22 ሕዝ10፥1
1፥24 2ነገ7፥6፤ መዝ46፥3፤ሕዝ3፥13፤ 10፥5፤43፥2፤ ዳን 10፥6፤ራዕ1፥15፤ 14፥2፤19፥6
1፥26 ቍ5፤ ዘፀ24፥10፤ 1ነገ22፥19፤ኢሳ6፥1፤ ኤር3፥17፤ሕዝ2፥1፤ ራእ1፥3
1፥27 ሕዝ8፥2
1፥28 ዘፍ9፥13፤ 17፥3፤ዘፀ16፥7፤ 24፥ 16፤ዘኍ14፥5፤ ሉቃ2፥9፤ራእ4፥2፤ 10፥1
2፥1 ኢዮ25፥6፤ መዝ8፥4፤ሕዝ1፥26፤ ዳን7፥13፤8፥15፤ 10፥11፤ሐሥ9፥6፤ 14፥10፤26፥16
2፥2 ሕዝ3፥24፤ ዳን8፥18
2፥3 ኤር3፥25፤ ሕዝ 5፥6፤ 20፥8-24፤24፥3
2፥4 ዘፀ32፥9፤ ኢሳ9፥9፤ሕዝ3፥7፤ አሞ7፥15
2፥5 ኤር5፥3፤ ሕዝ3፥11፡27፤ 33፥33፤ ዮሐ15፥22
2፥6 ዘኍ33፥55፤ ዘዳ31፥6፤2ነገ1፥15፤ ኢሳ1፥2፤9፥18፤ 30፥9፤ሕዝ24፥3፤ 44፥6፤ሚክ7፥4
2፥7 ኤር1፥7፤ 7፥27፤42፥21፤ ሕዝ 3፥10-11
2፥8 ዘኍ20፥10 -13፤መዝ81፥10፤ ኢሳ 8፥11፤50፥5፤ ኤር15፥16፤ራእ10፥9
2፥9 መዝ40፥7፤ ሕዝ 8፥3

1፥18 *በዐይኖች የተሞላ፤* እግዚአብሔር ሁሉን ማየት እንደሚችል የሚያመለክት ትእምርት ነው፡፡

1፥22 *ጠፈር፤* ይህ ቃል በዘፍ1፥6-8 ላይ ይገኛል፤ በዚህ ጠፈር በላይና በታች ያለው ውሃ ተለይቶአል፡፡ እዚህ ላይ ግን ፍጡራኑን ከእግዚአብሔር ክብር ለይተዋል፡፡

1፥26 *የሰው መልክ፤* ሕዝቅኤል በራእዩ የገለጸው እግዚአብሔርን ነው፤ ይሁን እንጂ አባባሉ፣ እግዚአብሔርን በቀጥታ እንዳልተመለከተ የሚገልጽ ነው (ዘፍ16፥13፤ ዘፀ3፥6፤ መሳ 13፥22 ይመ)፡፡

1፥28 *አምሳያ፤* የቍ26 ማብ ይመ፡፡ *የእግዚአብሔር ክብር፤* የእግዚአብሔር ክብር ትእምርታዊ በሆነ መልክ ሲገለጽ፣ ብሩህ ብርሃን ይመስላል (ዘፀ40፥34፤ ኢሳ6፥3 ይመ)፡፡ የእግዚአብሔርን ክብር በተመለከተ ያለው ግንዛቤ ከኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ ጋር ካለው ግንኙነት አንጻር ነው (1ነገ8፥11፤ መዝ 26፥8፤ 63፥2፤ 96፥6፤ 102፥16 ይመ)፡፡ በዚህ ጊዜ፣ እግዚአብሔር ቤተ መቅደሱን ትቶ በባቢሎን ሳለው ሕዝቡ መገለጡ፣ በሕዝቅኤል መልእክት ውስጥ የመጀመሪያ አጋማሽ ላይ የቀረበ ዋና ሐሳብ ነው (10፥4፤ 11፥23 ይመ)፡፡ ስለ ኢየሩሳሌም መታደስ ነቢዩ በተመለከተው ራእይ የእግዚአብሔር ክብር ወደ ኢየሩሳሌም ሲመለስ አይቶአል (43፥2)፡፡

2፥1 *የሰው ልጅ፤* ይህ አባባል በሕዝቅኤል መጽሐፍ 93 ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን፣ ከሁሉ በላይ የሆነ አምላክ ለነቢዩ መልእክቱን በሚያስተላልፍበት ጊዜ ነቢዩ ሰብአዊ ፍጡሩ መሆኑን በአጽንኦት ለማሳየት የተጠቀመበት ነው (የመዝ 8፥4 ማብ ይመ)፡፡ ከዚህ ሌላ፣ ይህ ሐረግ እንደ ማዕረግ ስም ሆኖ በብሉይ ኪዳን የተጠቀሰው በዳን7፥13 እና 8፥17 ላይ ነው፡፡ ኢየሱስ ስለ ራሱ በዚህ ስም በተደጋጋሚ መናገሩ፣ በዳን7፥13 ላይ በመጨረሻ እንደሚመጣ ተስፋ የተነገረለት መሢሕ እርሱ መሆኑን ለመግለጽ ነው (የማር 8፥31 ማብ ይመ)፡፡

2፥2 *መንፈስ ወደ ውስጤ ገብቶ በእግሬ አቆመኝ፤* ለሠረገሉቹ መንኰራኵሮችና (1፥12፡19፤ 10፥16-17) ፍጡራኑ ኀይል የሰጣቸው (1፥20) የእግዚአብሔር መንፈስ አሁን ደግሞ ለሕዝቅኤል የነቢይነት አገልግሎት ኀይል ሰጠው፡፡

2፥3 *ወደ ዐመፀኛው ... ሕዝብ፤* ይህ የሕዝቅኤል ስብከት መሪ ሐሳብ ሲሆን፣ በአጠቃላይ ይህ ሕዝብ በታሪኩ ሲታይ በእግዚአብሔር ላይ ዐመፀኛ እንደ ነበር ያመለክታል፡፡

2፥6 *ኵርንችትና እሾኽ ...ጊንጦች፤* እነዚህ የነቢዩን ሕይወት ችግር ላይ የሚጥሉ ሁኔታዎችን በግልጽ የሚያሳዩ ምስሎች ናቸው፡፡

2፥10 *ከፊትና ከኋላው፤* አብዛኛውን ጊዜ ጥንታዊ ጥቅል ጽሑፎች ከፊት ብቻ ይጻፍባቸው ነበር፡፡ በዚህ አኳኋን እዚህ ላይ መጻፉ፣ ጥቅልሉ መለኮታዊ ፍርድን የያዘ መሆኑን የሚያመለክት ነው (ዘካ5፥3 እና ራእ5፥1 ይመ)፡፡ *የሰቈቃ፣ የልቅሶና የዋይታ፤* ሕዝቅኤል በኋለኛው የአገልግሎት ጊዜው ተስፋ እንዳላቸው እንዲሰብክ ቢታዘዝም (የ33፥1 ማብ ይመ)፣ በመጀመሪያው

ብላና ሂደህ ለእስራኤል ቤት ተናገር" አለኝ:: [2]ስለዚህ አፌን ከፈትሁ፤ እርሱም መጽሐፉን አጐረሠኝ::

[3]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ እኔ የምሰጥህን ይህን ጥቅል መጽሐፍ ብላ፤ ሆድህንም ሙላ" አለኝ:: እኔም በላሁት፤ በአፌም ውስጥ እንደ ማር ጣፈጠኝ::

[4]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ተነሥተህ ወደ እስራኤል ቤት ሂድ፤ ቃሌንም ንገራቸው:: [5]ወደእስራኤል ቤት እንጂ፣ ንግግሩ ወደማይገባና ቋንቋው ወደማይታወቅ ሕዝብ አልተላክህም፤ [6]ንግግራቸው ወደማይገባና ቋንቋቸው ወደማይታወቅ፣ ቃላቸውንም መረዳት ወደማይቻልህ ብዙ ሕዝብ አልላክሁህም:: ወደ እነርሱ ልኬህ ቢሆን ኖሮ፣ በእርግጥ ይሰሙህ ነበር:: [7]ነገር ግን የእስራኤል ቤት ሁሉ ልበ ደንዳኖችና እልኸኞች ስለሆኑ ሊሰሙኝ አልፈለጉም፤ ስለዚህ የእስራኤል ቤት አንተንም አይሰሙህም:: [8]እነሆ እኔ በእነርሱ ፊት የማትበገር ጠንካራ አደርግሃለሁ:: [9]ግንባርህን ከባልጩት ይልቅ እንደሚጠነክር ድንጋይ አደርገዋለሁ:: ዐመፀኛ ቤት ቢሆኑም እንኳ አትፍራቸው፤ በፊታቸውም አትሸበር::"

[10]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ የምነግርህን ቃል ሁሉ በጥንቃቄ አድምጥ፤ በልብህም ያዝ:: [11]ተነሥተህም በምርኮ ወዳሉት ወገኖችህ ሂደህ ተናገራቸው፤ ቢሰሙህም ባይሰሙህም፣ '*ጌታ እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል' በላቸው::"

[12]*መንፈስም* ወደ ላይ ከፍ አድርጎ አነሣኝ፤ ከኋላዬም '*የእግዚአብሔር* ክብር በማደሪያ ስፍራው ይባረክ!' የሚል ታላቅ ህምህምታ ሰማሁ፤ [13]ይህም የሕያዋኑ ፍጡራን ክንፎች እርስ በርስ ሲጋጩና በአጠገባቸው ያሉት መንኰራኵሮች የሚያሰሙት ታላቅ ህምህምታ ነበር:: [14]*መንፈስ* ወደ ላይ ከፍ አድርጎ ወሰደኝ፤ እኔም በምሬትና በመንፈሴ ቍጣ ሄድሁ፤ *የእግዚአብሔርም* ጽኑ እጅ በላዬ ነበረች:: [15]ከዚያም በኮቦር ወንዝ አጠገብ በቴልአቢብ ወደሚኖሩት ምርኮኞች መጣሁ፣ በድንጋጤ ፈዝዤም ከእነርሱ ጋር ሰባት ቀን በመካከላቸው ተቀመጥሁ::

## ለእስራኤል የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

[16]ከሰባቱም ቀን በኋላ *የእግዚአብሔር* ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ፤ [17]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ለእስራኤል ቤት ጠባቂ አድርጌሃለሁ፤ ስለዚህ ቃሌን ስማ፤ የምነግርህንም ማስጠንቀቂያ አስተላልፍላቸው:: [18]እኔ ኀጢአተኛውን ሰው፣ 'በእርግጥ ትሞታለህ' ባልሁት ጊዜ አንተ ባታስጠነቅቀው፣ ነፍሱንም ያድን ዘንድ ከክፉ ሥራው እንዲመለስ ባትነግረው፣ ያ ኀጢአተኛ በኀጢአቱ[a] ይሞታል፤ አንተንም ስለ ደሙ በኀላፊነት እጠይቅሃለሁ:: [19]ነገር ግን ኀጢአተኛውን ሰው አስጠንቅቀኸው፣ ከኀጢአቱና ከክፉ መንገዱ ባይመለስ፣ እርሱ በኀጢአቱ ይሞታል፤ አንተ ግን ነፍስህን ታድናለህ::

[20]"ጻድቅ ሰው ደግሞ ከጽድቁ ተመልሶ ኀጢአት ቢሠራ፣ እኔም መሰናክል በፊቱ ባስቀምጥ እርሱ ይሞታል፤ አንተ ሳላስጠነቀቅኸውምና በኀጢአቱ ይሞታል፤ ያደረገውም ጽድቅ አይታሰብለትም፤ አንተንም ስለ ደሙ በኀላፊነት እጠይቅሃለሁ:: [21]ነገር ግን ጻድቁን ሰው ኀጢአት እንዳይሠራ ብታስጠነቅቀውና እርሱም ኀጢአትን ባይሠራ፣ ተጠንቅቆአልና በእርግጥ በሕይወት ይኖራል፤ አንተም ነፍስህን ታድናለህ::"

[a]18 *ወይም ስለ ኀጢአቱ፤ እንዲሁም* ቍ19 እና 20 ይመ

3፥3 መዝ19፥10፤ ኤር15፥16፤ ራእ10፥9-10
3፥4 ሕዝ11፥4:25
3፥5 ኢሳ28፥11፤ ዮና1፥2
3፥6 ዮና3፥5-10፤ ማቴ11፥21-23፤ ሐሥ 13፥46-48
3፥7 ኢሳ48፥4፤ ኤር3፥3፤7፥27፤ሕዝ 2፥4፤ዮሐ15፥20-23
3፥8 ኤር1፥18፤ 15፥20
3፥9 ኢሳ48፥4፤ 50፥7፤ኤር5፥3፤ሕዝ 2፥6፤44፥6፤ሚክ3፥8
3፥10 ኢዮ22፥22
3፥11 ቍ27፤ ኢሳ6፥9፤ሕዝ2፥4-5: 7፤11፥24-25
3፥12 ቍ14፤ሕዝ 8፥3፤43፥5
3፥13 ሕዝ1፥15:24፤ 10፥5:16-17
3፥14 ቍ12:22፤ 1ነገ18፥12፤ኢሳ8፥11፤ ሕዝ 37፥1
3፥15 ዘፍ50፥10፤ መዝ137፥1
3፥16 ኤር42፥7
3፥17 ኢሳ52፥8፤ 58፥1፤ኤር1፥17፤ ሕዝ11፥4፤ዕን2፥1
3፥18 ቍ20፤ዘፍ 2፥17፤ዮሐ8፥21:24
3፥19 ዘፍ6፥5፤ 2ነገ17፥13፤ መዝ7፥12፤ ኤር42፥16፤ ሕዝ14፥14:20፤ ሐሥ18፥6፤20፥26፤ 1ጢሞ4፥14-16
3፥20 ቍ18፤ ዘሌ26፥37፤ መዝ125፥5፤ኢሳ8፥14፤ ኤር34፥16፤ሕዝ7፥19፤ 18፥24፤ 33፥12:18
3፥21 ሐሥ20፥31

---

አገልግሎቱ ግን (ኢየሩሳሌም እስከፈረሰችበት ጊዜ ድረስ)፣ እግዚአብሔር በሕዝቡ እጅግ ማዘኑን፣ በኢየሩሳሌምና በመላው ይሁዳ ላይ ቍርጠኛ ፍርድ መወሰኑን ማወጁ ነበር::

3፥3 *በአፌም ውስጥ እንደ ማር ጣፈጠኝ፤* በነቢዩ ኤርምያስ ስሜት ውስጥ ተከሥቶ የነበረውን ነገር (ኤር15፥16)፣ ሕዝቅኤልም እንዲሁ ተለማምዶታል:: በውስጡ የያዘው መልእክት መራራ ቢሆንም (ራእ10፥9-10 ይመ)፣ የእግዚአብሔር ቃል ግን ለቀመሰው ጣፋጭ ነው (መዝ19፥10፤ 119፥103 ይመ)::

3፥6 *ወደ እነርሱ ልኬህ ቢሆን፤* ኢየሱስም ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ቃል፣ ለእስራኤል ተናግሮአል (ማቴ11፥21 ይመ)::

3፥9 *ግንባርህን ከባልጩት ይልቅ እንደሚጠነክር ድንጋይ አደርገዋለሁ፤* ስለ ፍርድ ለሚሰብክ ነቢይ፣ ብርታትና ጥንካሬ እጅግ አስፈላጊ መሣሪያዎች ናቸው:: እንዲሁም ነቢዩ ኤርምያስ የብርታትና የጥንካሬ መሣሪያዎችን ታጥቆ ነበር (ኤር 1፥18)::

3፥10 *በጥንቃቄ አድምጥ፣ በልብህም ያዝ፤* ነቢዩ፣ ከማያዳምጠው ሕዝብ ጋር ግልፅ በሆነ መንገድ ላይ እንደሚታይ ተደርጎ ተነጻጽሮአል::

3፥11 *በምርኮ ወዳሉት ወገኖችህ ሂደህ፤* የሕዝቅኤል አገልግሎት፣ እግዚአብሔር ኢየሩሳሌምንና ቤተ መቅደሷን እንደ ተወ ማመን ላልፈለገ በምርኮ ላለ ማኅበረሰብ ነበር:: ኢየሩሳሌም ከፈረሰች በኋላም ሕዝቡ ፈጽሞ ተስፋ ቈርጦ ነበር::

3፥14 *በምሬትና በመንፈሴ ቍጣ፤* ነቢዩ የእግዚአብሔርን የጽድቅ ቍጣ በመረዳት እርሱም በስሜቱ ከመለኮታዊው ስሜት ጋር በመተባበር ተቈጣ:: *የእግዚአብሔርም ጽኑ እጅ በላዬ ነበረች፤* የ1፥3 ማብ ይመ::

3፥15 *ቴልአቢብ፤* ምርኮኞች የሰፈሩበት የቦታ ስም የተገለጸው እዚህ ላይ ብቻ ነው:: የስሙም ትርጒም በባቢሎናውያን ቋንቋ፣ "የፍርስራሽ ወይም የጥፋት ክምር" ማለት ነው፤ ይህም፣ ስፍራው በፈራረሰ ሁኔታ ላይ ያለ መሆኑን ያመለክታል:: በአሁኑ ዘመን ካለችው ከእስራኤል ከተማ ስም ጋር ሲነጻጸር ግን፣ ትርጒሙ፣ "የእህል ኩረብታ" ማለት ነው:: *በድንጋጤ ... ሰባት ቀን፤* ሰዎች ከእግዚአብሔር ጋር ሲገናኙ እንደሚሆኑ፣ ሕዝቅኤልም ተመሳሳይ የሆነ መንፈሳዊ ሁኔታ እንደገጠመው ያመለክታል (ዕዝ9፥4፤ ኢዮ2፥13፤ 40፥4-5፤ ሐሥ9፥9 ይመ):: ሕዝቅኤል ከካህናት ቤተ ሰብ የተገኘ መሆኑን ግምት ውስጥ በማስገባት (የ1፥3 ማብ ይመ) የሰባቱ ቀን ጊዜ፣ አንድ ሰው ሥርዐተ ክህነት ለመቀበል የሚያስፈልገውን ጊዜ በትክክል ማሟላቱን ያመለክታል (ዘሌ8፥1-33)::

3፥17 *ጠባቂ አድርጌሃለሁ፤* ጥንት በእስራኤል፣ የከተማዪቱ ጠባቂዎች በከተማዪቱ ቅጥር ከፍ ያለ ቦታ ላይ ቆመው ይጠብቁ ነበር፤ ይህም በጦርነት ጊዜ የጦርነቱን ሁኔታ ለከተማዪቱ ነዋሪዎች ለመናገር (1ሳሙ14፥16)፣ ወይም በመምጣት ላይ ያሉ መልእክተኞችን ሁኔታ ለመናገር ያመች ነበር (2ሳሙ18፥24-27፤ 2ነገ9፥17-20):: ነቢያትም እንዲሁ፣ የእግዚአብሔርን ቃል ተቀብለው ለሕዝቡ የሚያስተላልፉ መንፈሳውያን ጠባቂዎች ናቸው (ኤር6፥17፤ ሆሴ9፥8፤ ዕን2፥1 ይመ):: በዚህ ስፍራ የሕዝቅኤል ጠባቂነት፣ የኢየሩሳሌምን አወዳደቅ ለመግለጽ ሳይሆን፣ የደረሰባቸው ነገር ሁሉ በእያንዳንዱ እስራኤላዊ ኀጢአት ምክንያት መሆኑን ለማሳሰብ ነው:: ይኸው ተልእኮ በ33፥7-9 በድጋሚ ተገልጾአል፤ በም18 ላይም በግልጽ ተጠቅሶአል::

[22]*የእግዚአብሔር* እጅ በላዬ ነበረ፤ እርሱም፣ “ተነሥተህ ወደ ረባዳው ስፍራ ሂድ፤ በዚያ እናገርሃለሁ” አለኝ:: [23]እኔም ተነሥቼ ወደ ረባዳው ስፍራ ሄድሁ:: በኮቦር ወንዝ አጠገብ ያየሁት ዐይነት ክብር፣ *የእግዚአብሔር* ክብር በዚያ ቆሞ ነበር፤ እኔም በግንባሬ ተደፋሁ::

[24]መንፈስ በውስጤ ገብቶ በእግሬ አቆመኝ፤ እንዲህም ሲል ተናገረኝ፤ “ሂድ፤ ቤትህ ገብተህ በርህን ዝጋ:: [25]አንተ፣ የሰው ልጅ ሆይ፤ በገመድ ይጠፍሩሃል፤ ወጥተህም በሕዝብ መካከል እንዳትመላለስ ያስሩሃል:: [26]ዐመፀኛ ቤት ቢሆኑም ልትገሥጻቸው እንዳትችል ምላስህን ከላንቃህ ጋር አጣብቃለሁ፤ ድዳም ትሆናለህ:: [27]ነገር ግን በምናገርህ ጊዜ አፍህን እከፍታለሁ፤ አንተም፣ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል’ ትላቸዋለህ:: የሚሰማ ይስማ፤ የማይሰማም አይስማ፤ ዐመፀኛ ቤት ናቸውና::

## የኢየሩሳሌም መከበብ ምሳሌ

**4** “አንተ፣ የሰው ልጅ ሆይ፤ አንድ የሸክላ ጡብ ወስደህ ከፊት ለፊትህ አስቀምጥ፤ የኢየሩሳሌምን ከተማ ካርታ ሥራበት:: [2]ከዚያም በወታደር እንደሚከበብ ክበባት፤ ምሽግ ሥራባት፤ ዐፈር ደልድልባት፤ ጦር ሰፈሮችን ቀብቅብባት፤ ቅጥር መደርመሻ ግንዶችንም በዙሪያዋ አስቀምጥባት:: [3]የብረት ምጣድ ወስደህ በአንተና በከተማዪቱ መካከል እንደ ብረት ቅጥር አቁመው፤ ፊትህንም ወደ እርስዋ አዙር፤ የተከበበች ትሆናለች፤ አንተም ትከባታለህ:: ይህም ለእስራኤል ቤት ምልክት ይሆናል::

[4]“አንተ በግራ ጐንህ ተኛ፤ የእስራኤልም ቤት ኀጢአት በአንተ ላይ[ñ] ይሁን፤ በዚህ ጐንህ በተኛህበት ቀን ቍጥር ኀጢአታቸውን ትሸከማለህ:: [5]እነርሱ ኀጢአት ባደረጉባቸው ዓመታት መጠን የቀን ቍጥር መድቤብሃለሁ:: ስለዚህ ሦስት መቶ ዘጠና ቀን የእስራኤልን ቤት ኀጢአት ትሸከማለህ::

[6]“ይህን ከፈጸምህ በኋላ ደግሞ በቀኝ ጐንህ ተኝተህ የይሁዳን ቤት ኀጢአት ትሸከማለህ፤ ለእያንዳንዱ ዓመት አንድ አንድ ቀን በማድረግ አርባ ቀን መድቤብሃለሁ:: [7]ፊትህን ወደ ኢየሩሳሌም ከበባ ታዞራለህ፣ በራቍት ክንድህ ትንቢት ተናገርባት:: [8]የከበባህን ወራት እስክትፈጽም ድረስ ከአንዱ ጐን ወደ ሌላው መገላበጥ እንዳትችል በገመድ አስርሃለሁ::

[9]“ስንዴና ገብስ፣ ባቄላና ምስር እንዲሁም ዘንጋዳና ጠመዥ ወስደህ በአንድ ሸክላ ውስጥ አስቀምጥ፤ ከዚያም ለራስህ እንጀራ ጋግር፤ ሦስት መቶ ዘጠና ቀን በጐንህ በምትተኛበት ጊዜ ትመገበዋለህ:: [10]በየቀኑ የምትበላውን እህል ሃያ ሃያ ሰቅል መዝነህ አስቀምጥ፤ በተወሰነ ጊዜ ትበላዋለህ፤ [11]የምትጠጣውንም ውሃ *አንድ ስድስተኛ ኢን ለክተህ አስቀምጥ፤ በተወሰነ ጊዜ ትጠጣዋለህ:: [12]የገብስ ዕንጎቻ እንደምትበላ አድርገህ ትበላለህ፤ የሰውንም ዐይነ ምድር አንድደህ በሕዝብ ፊት ጋግረው:: [13]*እግዚአብሔርም* “በዚህ ሁኔታ የእስራኤል ሕዝብ እነርሱን በምበትንበት በአሕዛብ መካከል ርኩስ ምግብ ይበላሉ” አለ::

[14]እኔም፣ “ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ወይኔ! ከቶ ረክሼ አላውቅም፤ ከልጅነቴ ጀምሮ እስከ ዛሬ ጥምብ ወይም አውሬ የገደለውን በልቼ አላውቅም፤ ርኩስ ሥጋም በአፌ አልገባም” አልሁ::

[15]እርሱም፣ “መልካም ነው፤ በሰው ዐይነ ምድር ሳይሆን፤ እንጀራህን በኩበት እንድትጋግር ፈቅጄልሃለሁ” አለኝ::

[16]ደግሞም እንዲህ አለኝ፤ “የሰው ልጅ ሆይ፤ የኢየሩሳሌምን የምግብ ምንጭ አደርቃለሁ፤ ሕዝቡም የተወሰነ ምግብ በጭንቀት ይበላል፤ የተመጠነ ውሃም በሥጋት ይጠጣል::

3+22 ቍ4፤ ሕዝ1+3፤8+4፤ ሐሥ9+6
3+23 ዘፍ17+3፤ ሕዝ1+1
3+24 ኤር15+17፤ ሕዝ2+2
3+25 ሕዝ4+8
3+26 መዝ22+15፤ ሕዝ2+5፤24+27፤ 33+22፤ሆሴ4+4
3+27 ቍ11፤ ሕዝ 2+5፤12+3፤ 24+27፤29+21፤ 33+22፤ራእ22+11
4+2 ኤር6+6፤ 33+4፤ሕዝ17+17፤ 21+22፤ዳን11+15
4+3 ቍ7፤ዘሌ2+5፤ ኢሳ8+18፤20+3፤ ኤር13+1-7፤18+1-4፤ 19+1-2፤39+1፤ ሕዝ5+1-4፤12+3-6፤ 20+46፤21+2
4+6 ዘፀ28+38፤ ዘኍ14+34፤ዳን9+24 -26፤12+11-12
4+7 ቍ3፤ ሕዝ6+2፤13+17
4+8 ሕዝ3+25
4+9 ኢሳ28+25
4+10 ዘፀ30+13
4+11 ቍ16
4+12 ኢሳ36+12
4+13 ሆሴ9+3፤ አሞ7+17
4+14 ዘፀ22+31፤ ዘሌ11+39፤ዘዳ14+3፤ 32+37-38፤ኤር1+6፤ ሕዝ9+8፤20+49፤ ዳን1+8፤ሆሴ9+3-4
4+16 ቍ10-11፤ ዘሌ26+26፤ መዝ105+16፤ኢሳ3+11 ሕዝ12+19

[ñ]4 ወይም *በአንተ በኩል ይሁን*
*አንድ ስድስተኛ (1/6ኛ) ኢን ግማሽ ሊትር ያህል ነው::

3+22 *የእግዚአብሔር እጅ፤* የ1+3 ማብ ይመ::

3+25 *በገመድ፤* ራሱ በገመድ መታሰሩን ሳይሆን፣ በሕዝብ መካከል አገልግሎቱን ለመስጠት አለመቻሉን ለመግለጽ ነው:: ይሁን እንጂ ሕዝቅኤል በራሱ ቤት ትንቢት ተናግሮአል (8+1)::

3+26 *ድዳም ትሆናለህ፤* በቍ 26-27 እንደ ተገለጸው፣ ነቢዩ የሚናገረውን ቃል ከእግዚአብሔር ካላገኘ በቀር ምንም አይናገርም:: አለመናገሩም፣ እስራኤላውያን የእግዚአብሔርን ቃል ለመቀበል አለመፈለጋቸውን ያመለክታል:: ይህ የሕዝቡ ሁኔታ የተሻሻለው ግን ከኢየሩሳሌም ውድቀት በኋላ ነው (24+27፤ 33+22):: ከዚህ በኋላ ግን በምርኮ ላሉት ወገኖቹ የሚናገረው መልእክት ከእግዚአብሔር ተሰጠው::

4+1 *የሸክላ ጡብ ወስደህ፤* ነቢዩ ሕዝቅኤል በትእምርት ከሚያቀርባቸው ከአያሌ አገላለጾች መካከል ይህ አንዱ ነው:: ሕዝቅኤል በባቢሎን የሚሠሩትን ርጥብ ሸክላዎች ዐይነት አበጅቶ የኢየሩሳሌምን ከተማ ካርታ ከሠራ በኋላ፣ ከተማዪቱ በወራሪ ኀይል መከበቧን ለመሳየት፣ ዙሪያዋን ምሽግ ይሠራብታል (ቍ2)፤ ከዚያም በእርሱና በሠራት ከተማ መካከል የብረት መጥበሻ (የምግብ ማብሰያ) አኖረ (ቍ3)፤ ይኸውም በከተማው ዙሪያ ያለው ምሽግ ሊሰበር የማይችል መሆኑን ለማመልከት ነው::

4+3 *አንተም ትከባታለህ፤* በዚህ ትዕይንት የሕዝቅኤል መገኘት፣ ከበባውን ያደረገው ራሱ እግዚአብሔር መሆኑን ለማመልከት ነው::

4+4 *ኀጢአታቸውን ትሸከማለህ፤* ኀጢአታቸውን የሚሸከመው፣ በምትክነት ሳይሆን በውክልና ነው:: የነቢዩ ድርጊት የእስራኤልን ኀጢአት በትእምርት የሚገልጽ እንጂ፣ ኀጢአታቸውን የሚያስወግድ አይደለም::

4+5 *ሦስት መቶ ዘጠና ቀን፤* እነዚህ ቀናት፣ ንጉሥ ሰሎሞን ታማኝነቱን ካጐደለበት ጊዜ ጀምሮ ኢየሩሳሌም እስከ ፈረሰችበት ጊዜ ድረስ ያለውን ሦስት መቶ ዘጠና ዓመታት ይወክላሉ፤ እንዲሁም በቍ6 ላይ የተጠቀሰው “አርባ ቀን” ክፉ የሆነው ምናሴ ንስሓ ከመግባቱ በፊት አርባ ዓመት የነገሠበትን ብዙ ዓመት ይወክላል (2ነገ21+11-15፤ 23+26-27፤ 24+3-4፤ 2ዜና33+12-13 ይመ)::

4+6 *በቀኝ ጐንህ፤* ነቢዩ ሕዝቅኤል አንድ ጊዜ በግራ ጐኑ፣ በሌላ ጊዜ ደግሞ በቀኝ ጐኑ በሸክላ በሠራት በኢየሩሳሌም ከተማ ላይ መተኛቱ የሰሜኑንና የደቡቡን መንግሥት ለማመልከት ነው::

4+9 *ስንዴና ገብስ፣ ባቄላና ምስር እንዲሁም ዘንጋዳና ጠመዥ፤* በተከበበች ከተማ ውስጥ ሊደርስ የሚችለውን የምግብ እጥረት የሚያመለክቱ ጥቂት የእህል ዐይነቶች ናቸው::

4+15 *ኩበት፤* በአሁኑም ጊዜ እንኳ፣ በመካከለኛው ምሥራቅ ምግብን ለማብሰል በማገዶነት ያገለግላል:: በሥርዐቱ መሠረት፣ ርኵስ ነገሮችን ላለመንካት ሕዝቅኤል እግዚአብሔርን ለመነ፤ እግዚአብሔርም በቸርነቱ በዐይነ ምድር ፈንታ የኩበት ማገዶ እንዲጠቀም ፈቀደለት::

17 የምግብና የውሃ ዕጥረት ስለሚኖር፣ እርስ በርስ ሲተያዩ ይደነግጣሉ፤ ከኀጢአታቸውም የተነሣ* መንምነው ይጠፋሉ።

**5** “አንተም፣ የሰው ልጅ ሆይ፤ የተሳለ ሰይፍ ወስደህ እንደ ጢም መላጫ ጠጕርህንና ጢምህን ተላጭበት፤ ጠጕሩንም በሚዛን ከፋፍል። 2 የከበባው ጊዜ ሲፈጸም የጠጕሩን ሢሶ በከተማው ውስጥ አቃጥለው፤ ሌላውን ሢሶ ጠጕር በከተማዪቱ ዙሪያ ሁሉ በሰይፍ ቈራርጠው፤ የቀረውንም ሢሶ ደግሞ ለነፋስ በትነው፤ እኔም በተመዘዘ ሰይፍ አሳድዳቸዋለሁና። 3 ደግሞም ከጠጕሮቹ ጥቂት ወስደህ በመጐናጸፊያህ ጫፍ ቋጥር፤ 4 እንደ ገናም ከእነዚህ ጥቂት ወስደህ እሳት ውስጥ ጨምራቸው፤ አቃጥላቸውም። እሳትም ከዚያ ወጥቶ ወደ እስራኤል ቤት ሁሉ ይሰራጫል።

5 “ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ‘አገሮችን በዙሪያዋ ሁሉ አድርጌ፣ በአሕዛብም መካከል ያስቀመጥኋት ኢየሩሳሌም ይህች ናት። 6 እርስዋም በዙሪያዋ ካሉት አገሮችና አሕዛብ ይልቅ በሕጌና በሥርዐቴ ላይ በክፋቷ ዐመፀች፤ ሕጌን ጥላለች፤ ሥርዐቴንም አልተከተለችም።’

7 “ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ‘በዙሪያችሁ ካሉት አሕዛብ ይልቅ ሞገደኞች ሆናችኋል፤ ሥርዐቴን አልተከተላችሁም፤ ለሕጌም አልታዘዛችሁም። በዙሪያችሁ የሚገኙ አሕዛብ የሚጠብቁትን ሕግ እንኳ አልጠበቃችሁም።[ሀ]

8 “ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ‘እነሆ፤ እኔ ራሴ በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤ በአሕዛብም ፊት ፍርድ አመጣብሻለሁ። 9 በጸያፍ ተግባርሽ ሁሉ ምክንያት ካሁን ቀደም ያላደረግሁትን፣ ወደ ፊትም የማላደርገውን በአንቺ ላይ አደርጋለሁ። 10 ስለዚህ በመካከልሽ አባቶች ልጆቻቸውን፣ ልጆችም አባቶቻቸውን ይበላሉ፤ ፍርድንም አመጣብሻለሁ፤ ከአንቺ የተረፉትንም ለነፋስ እበትናለሁ። 11 ስለዚህ በሕያውነቴ እምላለሁ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ መቅደሴን በረከሱ ምስሎችሽና በጸያፍ ተግባርሽ ሁሉ ስላጐደፍሽ፣ ፊቴን ከአንቺ እመልሳለሁ፤ በርኅራኄ አልመለከትሽም፤ አልምርሽም። 12 ከሕዝብሽ ሢሶው በቸነፈር ይሞታል፤ በመካከልሽም በራብ ያልቃል፤ ሌላው ሢሶ ከቅጥርሽ ውጪ በሰይፍ ይወድቃል፤ የቀረውን ሢሶ ደግሞ ለነፋስ እበትናለሁ፤ በተመዘዘም ሰይፍ አሳድደዋለሁ።

13 “ከዚያም ቍጣዬ ይበርዳል፤ በእነርሱ ላይ የመጣው መቅሠፍቴ ይመለሳል፤ ስበቀላቸው እረካለሁ፤ በእነርሱም ላይ መዓቴን ካወረድሁ በኋላ፣ እኔ እግዚአብሔር በቅናት እንደ ተናገርሁ ያውቃሉ።

14 “በዙሪያሽ ባሉ አሕዛብ መካከል፤ በአጠገብሽም በሚያልፉ ሁሉ ፊት ባድማና መሳለቂያ አደርግሻለሁ። 15 በቍጣና በመዓት፣ እንዲሁም በጭካኔ ፍርድ በማመጣብሽ ጊዜ፣ በዙሪያሽ ባሉ አሕዛብ ዘንድ የመሣቀያና የመሣለቂያ፣ የተግሣጽና የማስደንገጫ ምልክት ትሆኛለሽ። እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ። 16 የሚገድለውንና አጥፊ የሆነውን የራብ ፍላጻ በእናንተ ላይ በምወረውርበት ጊዜ በእርግጥ ሳጠፋችሁ እሰድዳለሁ። በራብ ላይ ራብ አመጣባችኋለሁ፤ የምግብ ምንጫችሁንም አደርቃለሁ። 17 ራብንና የዱር አራዊትን እሰድባችኋለሁ፤ እነርሱም ልጅ አልባ ያደርጓችኋል። ቸነፈርና ደም መፋሰስ ያጥለቀልቃችኋል፤ ሰይፍንም አመጣባችኋለሁ፤ እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ።”

## ስለ እስራኤል ተራሮች የተነገረ ትንቢት

**6** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 2 “የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ እስራኤል ተራሮች አዙር፤ ትንቢትም ተናገርባቸው፤ 3 እንዲህም በል፤ ‘የእስራኤል ተራሮች ሆይ፤ የጌታ የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ፤ ጌታ እግዚአብሔር ለተራሮችና

4፥17 ዘሌ26፥39፤ ሰቆ5፥4፤ ሕዝ5፥16፤ 12፥18-19፤ 24፥23፤ 33፥10፤ አሞ4፥8
5፥1 ዘሌ21፥5፤ ዘኍ6፥5፤ 2ሳሙ10፥4፤ ሕዝ44፥20
5፥2 ቍ10፡12፤ ዘሌ26፥33፤ ኤር9፥16፤ 13፥24፤ 21፥10፤ 39፥1-2፤ ሕዝ15፥7፤ ዘካ13፥8
5፥3 2ነገ25፥12፤ መዝ74፥11፤ ኤር39፥10
5፥4 ሕዝ10፥7፤ 15፥7
5፥5 ዘዳ4፥6፤ ሰቆ1፥1፤ ሕዝ16፥14
5፥6 2ነገ17፥15፤ ነህ9፥17፤ ኤር11፥10፤ ሕዝ2፥3፤ 16፥47-51፤ ዘካ7፥11
5፥7 2ነገ21፥9፤ 2ዜና33፥9፤ ኤር2፥10-11፤ ሕዝ16፥47
5፥8 ኤር21፥5፡13፤ 24፥9፤ ሕዝ11፥9፤ 15፥7፤ ዘካ14፥2
5፥9 ዳን9፥12፤ ማቴ24፥21
5፥10 ዘሌ26፥29፡ 33፤ መዝ44፥11፤ ኤር13፥14፤ ሰቆ2፥20፤ ሕዝ12፥14
5፥11 ዘፍ15፥2፤ ዘሌ15፥31፤ ዘኍ14፥21፤ 2ዜና36፥14፤ ኢዮ27፥22፤ ኤር16፥18፤ ሰቆ2፥17፤ ሕዝ7፥4፡ 9፡20፤ 8፥18፤ 9፥5፤ 11፥18
5፥12 ቍ2፡10፡17፤ መዝ107፥39፤ ኤር13፥24፤ 15፥2፤ 21፥9፤ ሕዝ6፥11-12፤ 7፥15፤ 12፥14፤ አሞ9፥4፤ ዘካ3፥8፤ ራእ6፥8
5፥13 2ዜና12፥7፤ ኢዮ20፥23፤ ኢሳ1፥24፤ 59፥17፤ ሕዝ16፥42፤ 21፥17፤ 24፥13፤ 38፥19፤ ሆሴ10፥10፤ ዘካ6፥8
5፥14 ዘሌ26፥32፤ ነህ2፥17፤ መዝ74፥3-10፤ 79፥1-4፤ ኢሳ64፥11፤ ሕዝ6፥6፤ 22፥4፤ ዳን9፥16፤ ሚክ3፥12

5፥15 ዘዳ28፥20፡ 46፤ 1ነገ9፥7፤ ኢሳ43፥28፤ ኤር22፥8-9፤ 24፥9፤ 23፥40፤ ሕዝ14፥8 5፥16 ዘሌ26፥26፤ ዘዳ32፥24 5፥17 ቍ12፤ ዘሌ 26፥25፤ ሕዝ14፥15፡ 21፤ 28፥23፤ 38፥22 6፥2 ቍ13፤ ሕዝ 4፥7፤ 18፥6፤ ሚክ6፥1 6፥3 ዘሌ26፥30፤ ሕዝ36፥4

*17 *ወይም በኀጢአታቸው መንምነው ይጠፋሉ*

ሀ7 አብዛኞቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆችና አንዳንድ የዕብራይስጥና የሱርስት የጥንት ቅጆች *የሚጠብቁትን ሕግ ጠብቃችኋል* ይላሉ።

5፥1 *የተሳለ ሰይፍ ወስደህ፤* ኢሳይያስ በተለዋጭ ዘይቤ የተጠቀመበትን አገላለጽ (ኢሳ7፥20)፣ ሕዝቅኤል በትንቢታዊ ትእምርት ተግባራዊ አደረገው።

5፥5 *ኢየሩሳሌም ይህች ናት፤* ሕዝቅኤል እስከ አሁን ምንም ቃል ሳይናገር ትእምርቶችን በተግባር ብቻ ሲገልጽ ቆይቶ ከ4፥1 ጀምሮ ከመለኮት ባገኘው መረዳት ስለ ኢየሩሳሌም መናገር ጀመረ።

5፥8 *እኔ ራሴ በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤* ሕዝቅኤል የእግዚአብሔርን ፍርድ ለማመልከት አብዛኛውን ጊዜ የሚጠቀምበት ግልጽና አጭር ሐረግ ነው (13፥8፤ 21፥3፤ 26፥3፤ 28፥22፤ 29፥3፡10፤ 30፥22፤ 34፥10፤ 35፥3፤ 38፥3፤ 39፥1 ይመ፤ በተጨማሪም ኤር23፥30-32፤ 50፥31፤ 51፥25፤ ናሆ 2፥13፤ 3፥5 ይመ)።

5፥10 *አባቶች ልጆቻቸውን ... ይበላሉ፤* ጠላት በሚከባቸው ጊዜ ሰው ሰውን የሚበላበት ሁኔታ እንደሚከሠት የተነገረ ነው፤ ይህም ኪዳን ከማፍረሳቸው የተነሣ የሚመጣ ቅጣት ነው (ዘዳ28፥53፤ ኤር19፥9፤ ሰቆ2፥20፤ ዘካ11፥9 ይመ)።

5፥11 *እኔ ሕያው እግዚአብሔርን! በራሴ እምላለሁ፤* የ18፥3 ማብ ይመ።

5፥13 *መዓቴን ከአወረድሁ በኋላ፤* በዚህ መጽሐፍ እግዚአብሔር በተደጋጋሚ የተናገረው ጠንከር ያለ አገላለጽ ነው (6፥12፤ 7፥8፤ 13፥15፤ 20፥8፡21 ይመ)። *እኔ እግዚአብሔር ... እንደ ተናገርሁ ያውቃሉ፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ፣ በዚህ ሁኔታ ከቀረቡት ስልሳ አምስት አባባሎች መካከል ይህ የመጀመሪያው ነው፤ የእግዚአብሔር መፍረድና ማዳን፣ ማንነቱን በግልጽ ያሳያል፤ ሕዝቡ የእግዚአብሔርን ቃል መስማት እስካልፈለገ ድረስ ትምህርት የሚሆነውን ነገር የሚያገኘው ከሚሰነዘርበት የቅጣት በትር ነው።

5፥15 *የመሣቀያና የመሣለቂያ፣ የተግሣጽና የማስደንገጫ ምልክት ትሆኛለሽ፤* አራት የቅጣት ዐይነቶች ናቸው (የ1፥5 ማብ ይመ)።

ለኰረብቶች፣ ለገደላገደሎችና ለሸለቆች እንዲህ ይላል፤ "ሰይፍን አመጣባችኋለሁ፤ የማምለኪያ ኰረብቶቻችሁን አጠፋለሁ:: 4መሠዊያዎቻችሁ ይፈርሳሉ፤ የዕጣን መሠዊያዎቻችሁም ይሰባበራሉ፤ የታረዱ ሰዎቻችሁን በጣዖቶቻችሁ ፊት እጥላለሁ:: 5የእስራኤላውያንን ሬሳ በጣዖቶቻችሁ ፊት አጋድማለሁ፤ ዐጥንቶቻችሁንም በመሠዊያዎቻችሁ ዙሪያ እበትናለሁ:: 6መሠዊያዎቻችሁ እንዲፈራርሱና እንዲወድሙ፣ ጣዖቶቻችሁ እንዲሰባበሩና እንዲደቁ፣ የዕጣን መሠዊያዎቻችሁ እንዲንኰታኰቱ፣ የእጆቻችሁም ሥራ እንዲደመሰስ፣ የምትኖሩባቸው ከተሞች ሁሉ ባድማ ይሆናሉ፤ ማምለኪያ ኰረብቶችም እንዳልነበሩ ይሆናሉ:: 7የታረዱ ሰዎቻችሁ በመካከላችሁ ይወድቃሉ፤ እኔም እግዚአብሔር እንደሆንሁ ታውቃላችሁ::"

8"በአሕዛብ መካከል ስትበተኑ፣ አንዳንዶቻችሁ ከሰይፍ ታመልጣላችሁና፣ ጥቂት ሰዎችን አስቀራለሁ:: 9እነዚህ ከሰይፍ የተረፉት፣ ከእኔ ዘወር ባለ አመንዝራ ልባቸውና ጣዖትን በተከተለ አመንዝራ ዐይናቸው የቱን ያህል እንዳሳዘኑኝ፣ በአሕዛብ ምድር ሆነው ያስታውሱኛል፤ ካደረጉት ክፋትና ከፈጸሙት ርኩስ ተግባር ሁሉ የተነሣም ራሳቸውን ይጸየፋሉ:: 10እነርሱም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ፤ ይህንም ክፉ ነገር አመጣባቸዋለሁ ብዬ የተናገርሁት በከንቱ አይደለም::

11" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "የእስራኤል ቤት ካደረጉት ክፋትና ከፈጸሙት ጸያፍ ተግባራቸው ሁሉ የተነሣ በሰይፍ በራብና በቸነፈር ይወድቃሉና፤ በእጅህ እያጨበጨብህ በእግርህም መሬት እየረገጥህ፣ 'ወየው!' ብለህ ጩኽ:: 12በሩቅ ያለው በቸነፈር ይሞታል፤ በቅርብ ያለው በሰይፍ ይወድቃል፤ በሕይወት የተረፈውና የዳነው በራብ ያልቃል:: መዓቴንም በዚህ ዐይነት ሁኔታ በእነርሱ ላይ እፈጽማለሁ:: 13የታረዱት ሰዎቻቸው በመሠዊያው ዙሪያ በጣዖቶቻቸው መካከል፣ ከፍ ባሉ ኰረብቶች ሁሉና በተራሮች ዐናት ሁሉ ላይ፣ በለመለመ ዛፍ ሁሉና ቅጠሉ በበዛ ወርካ ሁሉ ሥር፣ በአጠቃላይ ለጣዖቶቻቸው ጣፋጭ ሽታ ያለውን ዕጣን ባቀረቡበት ስፍራ ሁሉ ተጥለው ሲታዩ፣ ያን ጊዜ እኔ እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ:: 14እጄን በእነርሱ ላይ እነሣለሁ፤ የሚኖሩበትንም ስፍራ ከምድረ በዳው እስከ ዴብላታ+ ድረስ ምድሪቱን ባድማ አደርጋታለሁ፤ ያን ጊዜም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::"

## ፍጻሜው ደረሰ

7 የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 2"አንተ የሰው ልጅ ሆይ፤ ጌታ እግዚአብሔር ለእስራኤል ምድር እንዲህ ይላል፤ 'ፍጻሜ! በአራቱም የምድሪቱ ማእዘን ፍጻሜ መጥቶአል:: 3አሁንም መጨረሻሽ ደርሶአል፤ ቍጣዬን በአንቺ ላይ እፈሳለሁ፤ እንደ አካሄድሽ እፈርድብሻለሁ፤ ስለ ጸያፍ ተግባርሽ ሁሉ ተገቢውን ቅጣት እከፍልሻለሁ:: 4በርኅራኄ ዐይን አልመለከትሽም፤ ምሕረትም አላደርግልሽም፤ ስለ አካሄድሽና በመካከልሽ ስላለው ጸያፍ ተግባር ተገቢውን ቅጣት እከፍልሻለሁ፤ በዚያ ጊዜ እኔ እግዚአብሔር እንደሆንሁ ታውቃላችሁ ::'

5"ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'መዓት! ተሰምቶ የማይታወቅ መዓት* ይመጣል:: 6ፍጻሜ መጥቶአል! ፍጻሜ መጥቶአል! በአንቺ ላይ ተነሥሥቶአል፤ እነሆ፤ ደርሶአል! 7እናንት በምድሪቱ የምትኖሩ ሆይ፤ የጥፋት ፍርድ መጥቶባችኋል፤ ጊዜው ደርሶአል፤ በተራሮች ላይ እልልታ ሳይሆን ሽብር የሚሰማበት ቀን ቀርቦአል:: 8እነሆ፤ መዓቴን በቅርብ ቀን አፈስብሻለሁ፤ በአንቺ ላይ ቍጣዬን እፈጽምብሻለሁ፤ እንደ አካሄድሽ እፈርድብሻለሁ፤ ስለ ጸያፍ ተግባርሽም ሁሉ

6+4 2ዜና14+5፤ ሕዝ9+6፤14+13፤ 20+16
6+5 ቍ13፤ዘሌ26+30፤ዘኍ19+16፤ መዝ53+5፤ኤር8+1-2
6+6 ዘፀ12+20፤ዘሌ 26+30፤1ሳሙ5+4፤ ኢሳ6+11፤ሕዝ5+14 ፤ሕዝ30+13፤ ሆሴ10+8፤ሚክ1+7፤ ዘካ13+2
6+7 ቍ10:13:14፤ ሕዝ9+7፤11+10-12
6+8 ዘፍ11+4፤ መዝ44+11፤68+20፤ ኢሳ6+13፤ኤር44+14: 28፤ሕዝ7+16፤12+16፤ 14+22
6+9 ዘፀ22+20፤ 32+22፤ኢዮ42+6፤ መዝ137+6፤ ኢሳ7+13፤ኤር8+21፤ ሕዝ20+7:24:43፤ 23+14-16፤36+31፤ ሚክ5+13፤ዘካ10+9
6+10 ቍ7፤ ዘጸ28+52፤ኤር40+2
6+11 ኤር42+22፤ ሕዝ21+14:17፤ 22+13፤25+6
6+12 ኢዮ20+23፤ ሕዝ5+12፤7+15
6+13 ዘሌ26+30፤ 1ነገ14+23፤ኢሳ 1+29፤ኤር2+20፤ ሕዝ18+6፤20+28፤ ሆሴ4+13
6+14 ዘፀ7+5፤ኢዮ 30+21፤ኤር6+12፤ 51+25፤ሕዝ12+19፤ 14+13፤20+34
7+2 አሞ8+2:10፤ ራእ7+1፤20+8
7+3 ዘፍ6+13፤ ሕዝ18+30
7+4 ኤር13+14፤ ሕዝ5+11፤23+49
7+5 2ነገ21+12
7+6 ሕዝ39+8
7+7 ኢዮ18+20፤ ኢሳ2+12፤ሕዝ12+23፤ 30+3፤አሞ5+18-20፤ ሶፎ1+14፤ሚል3+2
7+8 ኢሳ42+25፤ ሕዝ9+8፤14+19፤ 20+8:21፤22+22፤

+14 አብዛኞዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች እንዲሁ ናቸው፤ ጥቂት የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ግን *ሪብላህ* ይላሉ
*5 አብዛኞዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች እንዲሁ ናቸው፤ አንዳንድ የዕብራይስጥና የሱርስት የጥንት ቅጆች ግን *በጥፋት ላይ ጥፋት* ይላሉ

6+3 *የማምለኪያ ኰረብቶቻችሁ፤* ሥር መሠረታቸው ከከነዓናውያን የሆኑና በሜዳ ላይ የአምልኮ ሥርዐት የሚፈጸምባቸው ቤተ ጣዖታት ናቸው፤ እነዚህም በብሉይ ኪዳን መጽሐፍ ሁሉ የተወገዙ ናቸው:: እነዚህ የማምለኪያ ኰረብታዎች፣ "ከመሠዊያዎች"፣ "ከዕጣን መሠዊያዎችና" "ከጣዖታት" ጋር (ቍ4)፣ አራት ከአምልኮ ጋር ግንኙነት ያላቸውን ነገሮች ያመለክታሉ (የ1+5 ማብ ይመ)::

6+4 *የዕጣን መሠዊያዎቻችሁም፤* ግማሽ ሜትር ያህል ከፍታ ያላቸውና አብዛኛውን ጊዜ የእንስሳት ወይም የከነዓናውያን አማልክት ምስል የተቀረጸባቸው ከሸክላ የተሠሩ ናቸው:: *ጣዖቶቻችሁ፤* ይህ ቃል፣ በዕብራይስጥ የማንኳሰስ ቃል ነው (በቍሙ "ድቡልቡል ፍግ" ማለት ነው):: ይህ አባባል በሕዝቅኤል መጽሐፍ 38 ጊዜ፣ በሌላ የብሉይ ኪዳን መጽሐፍ 9 ጊዜ ብቻ ተጠቅሶ ይገኛል::

6+9 *የተረፉት ... ያስታውሱኛል፤* ከሚያመጣው ፍርድ ያመለጡትን ያመለክታል (ቍ10 ይመ)::

6+11 *በእጅህ እያጨበጨብህ፤* ስለ ኀጢአታቸው በእስራኤል ጠላቶች ላይ በእስራኤላውያን ላይ የሚደርሰው ፍርድ በእነርሱ ላይም ቢደርስባቸውም፣ ይህ ትእዛዝ የሚመጣው ፍርድ (25+6 ይመ)፣ በሕዝቅኤልም ላይ እንደሚደርስ የሚያመለክት ነው::

6+14 *እጄን በእነርሱ ላይ እነሣለሁ፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ በተደጋጋሚ የቀረበ ሐረግ ነው (14+9:13፤ 16+27፤ 25+7፤ 35+3 ይመ):: *ዴብላታ፤* ምናልባት በኤር 48+22 ስሟ የተጠቀሰው የሞዓብ ከተማ ቤት ዲብላታይም ወይም ከደማስቆ በአሮንቴ በስተሰሜን በጸሮንቴ ወንዝ አጠገብ የምትገኘው ሪብላ ልትሆን ትችላለች::

7+2 *በአራቱም የምድሪቱ ማእዘን፤* እግዚአብሔር በእስራኤል ምድር ላይ የሚያመጣው ፍርድ ዓለም በሙሉ ያዳርሳል (የ1+5 ማብ ይመ)::

7+7 *ቀን፤* የጌታ ቀን የተባለው ነው:: ከአሞጽ ጀምሮ (አሞ 5+18-20)፣ በአብዛኞዎቹ ነቢያት ዘንድ ይህ ቀን ታላቅ የፍርድ ቀን እንደሆነ ይታመናል፤ ቀኑ (በዚህ ቦታ ላይ እንደ ተጠቀሰው ባይሆንም) የእግዚአብሔርን ሕዝብ የሚያስጨንቍ ጠላቶች ተጠራርገው የሚወገዱበትና ሰላም የሚገኝበት የፍርድ ቀን ነው ተብሎ ይታመናል:: *እልልታ ሳይሆን ሽብር፤* ከአሞ 5+20 ጋር ያነጻጽሩ ("ጨለማ እንጂ ብርሃን አይደለም" ማለት ነው)::

7+8 *መዓቴን ... አፈስብሻለሁ፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ በተደጋጋሚ የተነገረ ሐረግ ነው:: (9+8፤ 14+19፤ 20+8: 13:21፤ 22+31፤ 30+15፤ 36+18 ይመ)::

ተገቢውን ቅጣት እከፍልሻለሁ:: [9]በርኅራኄ ዐይን አልመለከትሽም፤ ምሕረት አላደርግ ልሽም፤ ስለ አካሄድሽና በመካከልሽ ስላለው ጸያፍ ተግባር ተገቢውን ቅጣት እከፍል ሻለሁ፤ በዚያ ጊዜ፣ የምቀሥፍ እኔ እግዚ አብሔር መሆኔን ታውቃላችሁ::

[10]" 'እነሆ ቀኑ! ይኸው ደረሰ! የጥፋት ፍርድ ተገልጦአል፤ በትሩ አቈጥቍጦአል፤ ትዕቢት አብቦአል:: [11]ዐመፅ አድጋ የክፋት በትር ሆነች፤ ከሕዝቡ አንድም አይተርፍም፤ ከሰዎቹ፣ ከሀብታቸውና እርባና ካለው ነገር አንዳች አይቀርም:: [12]ጊዜው ደርሶአል፤ ቀኑም ይኸው! መዓት በሕዝቡ ሁሉ ላይ ስለ መጣ፣ የሚገዛ አይደሰት፤ የሚሸጥም አይዘን:: [13]ሁለቱ በሕይወት እስካሉ ድረስ ሻጩ የሸጠውን መሬት አያስመልስም፤ ስለ መላው ሕዝብ የተነገረው ራእይ አይለወጥምና:: ከኀጢአ ታቸው የተነሣ ሕይወቱን ማትረፍ የሚችል አንድም አይገኝም:: [14]መለከት ቢነፉም፣ ሁሉንም ነገር ቢያዘጋጁም፣ ወደ ጦርነት የሚሄድ አንድ እንኳ አይኖርም፤ መዓቴ በሕዝብ ሁሉ ላይ መጥቶአልና::

[15]"በውጭ ሰይፍ፣ በውስጥ ደግሞ ቸነፈርና ራብ አለ፤ በገጠር ያሉት በሰይፍ ይወ ድቃሉ፤ በከተማ ያሉትም በራብና በቸነፈር ያልቃሉ:: [16]ተርፈው ያመለጡት ሁሉ በሸ ለቆ እንደሚኖሩ ርግቦች ስለ ኀጢአታቸው እያለቀሱ በተራራ ላይ ይሆናሉ:: [17]እጅ ሁሉ ይዝላል፤ ጕልበት ሁሉ ውሃ ይሆናል:: [18]ማቅ ይለብሳሉ፤ ሽብርም ይውጣቸዋል:: ፊታቸው ኀፍረት ይለብሳል፤ ራሳቸውም ይላጫል:: [19]ብራቸውን በየጐዳናው ይጥላሉ፤ ወርቃቸውም እንደ ርኩስ ነገር ይቈጠራል:: በእግዚአብሔር የቍጣ ቀን ብራቸውና ወርቃቸው ሊያድናቸው አይችልም፤ በኀጢ አት እንዲወድቁ ዕንቅፋት ሆኖባቸዋልና በልተው አይጠግቡበትም፤ ሆዳቸውንም አይሞ ሉበትም:: [20]በውብ ዕንቍቻቸው ታበዩዋል፤ ይህንም አስጸያፊ የጣዖት ምስሎቻቸውንና ርኩስ ቅርጻ ቅርጾችን ለመሥራት ተጠቅ መውበታል:: ስለዚህ እነዚህን ነገሮች ወደ ርኩሰት እለውጥባቸዋለሁ:: [21]ለባዕዳን ዝርፊያ፣ ለምድር ክፉዎችም ብዝበዛ አድርጌ አሳልፌ እሰጣለሁ፤ እነርሱም ያረክሱታል:: [22]ፊቴን ከእነርሱ እመልሳለሁ፤ እነርሱም የከበረውን ቦታዬን ያረክሳሉ፤ ወንበዴዎች ይገቡበታል፤ ያረክሱታልም::

[23]" 'ምድር በደም መፋሰስ፣ ከተማዪቱም በዐመፅ ተሞልታለችና ሰንሰለት አዘጋጅ:: [24]እጅግ የከፋትን ከአሕዛብ አምጥቼ ቤቶቻ ቸውን እንዲነጥቁ አደርጋለሁ፣ የኀያላኑንም ትዕቢት አጠፋለሁ፤ መቅደሳቸውም ይረክ ሳል:: [25]ሽብር በመጣ ጊዜ ሰላምን ይሻሉ፤ ነገር ግን አያገኙትም:: [26]ጥፋት በጥፋት ላይ፣ ወሬም በወሬ ላይ ይመጣል:: ራእይን ከነቢይ ለማግኘት ይጥራሉ፤ የሕግ ትምህርት ከካህኑ፣ ምክርም ከሽማግሌው ዘንድ ይጠ ፋል:: [27]ንጉሡ ያለቅሳል፤ መስፍኑ ተስፋ መቍረጥን ይከናነባል፤ የምድሪቱም ሕዝብ እጅ ትንቀጠቀጣለች:: የእጃቸውን እከፍላ ቸዋለሁ፤ ራሳቸው ባወጡት መስፈርት መሠ ረት እፈርድባቸዋለሁ:: በዚያ ጊዜ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::' "

## ባዕድ አምልኮ በቤተ መቅደስ

**8** በስድስተኛው ዓመት፣ በስድስተኛው ወር፣ በአምስተኛው ቀን በቤቴ ተቀምጬ ሳለሁ፣ የይሁዳም ሽማግሌዎች በፊቴ ተቀምጠው ሳሉ፣ በዚያ የጌታ እግዚአብሔር እጅ በላዬ መጣች:: [2]እኔም አየሁ፤ እነሆ፣ የሰውን ልጅ የሚመስል ነበረ፤ ወገቡ ከሚመስለው በታች እንደ እሳት ያለ ነበር፤ ወገቡንም ከሚመስለው ጀምሮ ወደ ላይ እንደ ጋለ

36፥19፤ሆሴ5፥10፤ ናሆ1፥6
7፥9 ዘዳ32፥35፤ መዝ39፥10፤ኢሳ 9፥13፤ኤር21፥7፤ ሕዝ5፥11፤22፥31
7፥10 መዝ89፥32፤ ኢሳ10፥5
7፥11 መዝ55፥9፤ ኢሳ58፥4፤ኤር16፥6 ፤ሶፎ1፥18
7፥12 ቍ7፤ኢሳ 5፥13-14፤24፥2፤ ሕዝ30፥3
7፥13ዘሌ25፥24-28
7፥14 ኢዮ39፥24፤ ኤር25፥38
7፥15 ዘዳ32፥25፤ ኤር14፥18፤ሰቆ1፥20 ፤ሕዝ5፥12፤33፥27
7፥16 ዘፍ8፥8፤ዕዝ 9፥15፤ኢሳ10፥20፤ 59፥11፤ኤር9፥19፤41 ፥16፤42፥17፤ ሕዝ6፥8
7፥17 2ነገ19፥26፤ ኤር47፥3፤ሕዝ21፥7፤ 22፥14፤ዳን5፥6
7፥18 መዝ55፥5፤ ኢሳ15፥2-3፤ኤር4፥8 ፤8፥37፤49፥3፤ሕዝ 27፥31፤አሞ8፥11
7፥19ምሳ11፥4፤ኢሳ 42፥25፤55፥2፤ሰቆ4፥ 1፤ሕዝ3፥20፤13፥5፤ 14፥3፤30፥3፤ሆሴ4፥ 5፤ኢል1፥15፤2፥1፤ ሶፎ1፥7፡18፤2፥2
7፥20 ኢሳ2፥20፤ 30፥22፤ኤር10፥3፤ ሕዝ5፥11፤16፥17
7፥21 ዘኍ14፥3፤ 2ነገ24፥13
7፥22 መዝ74፥7-8 ፤ኤር2፥27፤19፥13፤ ሰቆ2፥7፤ሕዝ39፥23-24
7፥23 ዘፍ6፥11፤ 2ነገ21፥16፤ኢሳ1፥15 ፤ሕዝ11፥6፤22፥9
7፥24 2ዜና7፥20፤ሰቆ2፥7፤ ሕዝ24፥21፤28፥7
7፥25 ኤር6፥14፤ 8፥11፤ሕዝ13፥10፡16

7፥26 ዘዳ29፥21፤ 31፥17፤1ሳሙ3፥1፤ኢሳ47፥11፤ኤር18፥18፤ ሕዝ20፥1-3፤ አሞ8፥11፤ሚክ3፥6 7፥27 ቍ4፤መዝ 109፥19፤ ኢሳ3፥11፤ሕዝ18፥20፤26፥16 8፥1 2ነገ6፥32፤ ሕዝ1፥1-3፤ 14፥1፤ 24፥1፤33፥31፤40፥1 8፥2ሕዝ1፥4፡26-27

11 ወይም *ዐመፀኛው የክፋት በትር*
2 ወይም *እሳት የሚመስል አየሁ*

7፥12 *የሚገዛ አይደሰት፤* ኢየሱስ ክርስቶስ ስለ መጨረ ሻው ዘመን ከተናገረው ጋር የሚመሳሰል ነው (ማቴ24፥17-18 ይመ):: ሕዝቡ ተማርኮ መሄዱ የማይቀር ጕዳይ ስለ ሆነ፣ የሚገዛ ሰው ባገኘው ንብረት መደሰት አለመቻሉን፣ የሚሸጥም ንብረቴን አጣሁ ብሎ ማዘን እንደሌለበት የሚያሳስብ ምክር ነው::

7፥19 *ብራቸውን ... ይጥላሉ፤* ኢሳ2፥20 ይመ::

7፥20 *በውብ ዕንቍቻቸው፤* ዘፀ32፥2-4 ይመ::

7፥22 *የተከበረውን ቦታዬን፤* የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅደስ ነው::

7፥24 *የኀያላኑንም ትዕቢት፤* በ24፥21፤ 33፥28 ላይ የኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ፣ "ትዕቢት" በሚል ቃል ተገልጾአል::

7፥26 *ነቢይ ... ካህን ... ሽማግሌ፤* ከእግዚአብሔር ዘንድ ምሪት የለም፤ መሪዎችም አቅጣጫ ሊያመለክቱ አልቻሉም (1ሳሙ 28፥6፤ አሞ8፥11-12 ሚክ3፥6-7 ይመ)::

7፥27 *ንጉሡ ... መስፍኑ፤* እዚህ ላይ፣ ሁለቱም ሰዎች የሚያመለክቱት አንዱን ሰው ነው:: ሕዝቅኤል ዮአኪንን ንጉሥ (1፥2)፣ ሴዴቅያስን ግን የሚቈጥረው እንደ መስፍን አድርጎ ነው (12፥12):: *የምድሪቱም ሕዝብ፣* ርስት ያለውንና በሰራዊቱ ውስጥ የሚያገለግለውን፣ የይሁዳ ነዋሪ ሁሉ ነው (ከ12፥19፤ 45፥16፡22፤ 46፥3 ጋር ያነጻጽሩ)::

8፥1-11፥25፤ በእነዚህ አራቱ ምዕራፎች ውስጥ ያለው ራእዩ የሚያመለክተው የእግዚአብሔር ክብር ቤተ መቅደስ የእግ ዚአብሔር ክብር ከረከሰው ቤተ መቅደስ ለቆ መሄዱን ነው (8፥4፤ 9፥3፤ 10፥18-19፤ 11፥23 ይመ)::

8፥1 *በስድስተኛው ዓመት፣ በስድስተኛው ወር፣ በአምስ ተኛው ቀን፤* መስከረም 17/592 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው፤ ይህ ጊዜ፣ ነቢዩ ሕዝቅኤል ከጠቀሳቸው ዐሥራ ሦስት ቀናት መካከል ሁለተኛው ነው:: ይኸኛውም በ1፥2 እና በ40፥1 ላይ እንደ ተጠ ቀሰው አንዱን ራእይ ያመለክታል:: *በቤቴ ተቀምጬ፤* በምርኮ የሄዱት የራሳቸውን ቤት መሥራት ችለው ነበር (ኤር29፥5):: *የይሁዳም ሽማግሌዎች በፊቴ ተቀምጠው ሳሉ፤* በምርኮ የሄዱት ሰዎች ከቦታ ቦታ የመንቀሳቀስ፣ የመሰብሰብና የአምልኮ ነጻነት ነበራቸው:: የመጀመሪያውን ራእይ ከተቀበለና ለሕዝቡ ከሰበከ ከአንድ ዓመት ከሁለት ወር በኋላ፣ እግዚአብሔር እንደ ገና ለነቢዩ ተናገረው:: አንዳንዶች፣ በነቢዩ በሕዝቅኤል ቤት የተደ ረገውን ይህን ስብሰባ፣ የምኵራብ አምልኮ ጅማሬ ነው ይላሉ:: *የልዑል እግዚአብሔር እጅ፤* የ1፥3 ማብ ይመ::

8፥2 *የሰውን ልጅን የሚመስል፤* ገጽታው በ1፥26-27 ላይ የተገለጸውን የአምላክን ገጽ የሚመስል መልአክ ነው:: *እንደ እሳት ... እንደ ጋለ ብረት ያበራ ነበር፤* ብርሃኑ የሚያንፀባርቅና

ብረት ያበራ ነበር። [3]እርሱም እጅ መሳይ ዘርግቶ የራስ ጠጕሬን ያዘ፤ መንፈስም በምድርና በሰማይ መካከል አነሣኝ፤ እርሱም ቅናት የሚያነሣው ጣዖት ወደ ቆመበት፣ ወደ ውስጠኛው አደባባይ መግቢያ ወደ ሰሜን በር ወደ ኢየሩሳሌም በእግዚአብሔር ራእይ ወሰደኝ። [4]እነሆ፤ በረባዳው ስፍራ በራእይ ያየሁት የእስራኤል አምላክ ክብር በዚያ ነበረ።

[5]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ወደ ሰሜን ተመልከት" አለኝ። እኔም ተመለከትሁ፤ እነሆ ከመሠዊያው በር በሰሜን በኩል መግቢያው ላይ ይህ የቅናት ጣዖት ነበረ።

[6]ደግሞም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ የእስራኤል ቤት ከመቅደሴ ያርቀኝ ዘንድ በዚህ የሚያደርገውን እጅግ አስጸያፊ ነገር ታያለህን? ከዚህም የባሰ አስጸያፊ ነገር ታያለህ" አለኝ።

[7]ከዚያም በኋላ ወደ አደባባዩ መግቢያ አመጣኝ፤ እኔም ግንቡን ተመለከትሁ፤ ቀዳዳም ነበረበት። [8]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ግንቡን ንደለው" አለኝ፤ እኔም ግንቡን ነደልሁት፤ አንድ በርም አገኘሁ።

[9]እርሱም፣ "ግባና በዚህ የሚፈጽሙትን እጅግ የከፋ ርኵሰት ተመልከት አለኝ። [10]እኔም ገብቼ አየሁ፤ እነሆ በደረታቸው የሚሳቡ ፍጡራንና የርኩሳን አራዊት ዐይነት ሁሉ፣ የእስራኤልም ቤት ጣዖታት ሁሉ ዙሪያውን በግንቡ ላይ ተቀርጸው ነበር። [11]በእነዚህም ፊት ከእስራኤል ቤት ሰባ ሽማግሌዎች ቆመው ነበር፤ በመካከላቸውም የሳፋን ልጅ ያእዛንያ ቆሞ ነበር፤ እያንዳንዳቸውም በእጃቸው ጥና ይዘዋል፤ መልካም መዐዛ ያለው የዕጣን ጢስም እየተትጐለጐለ ይወጣ ነበር።

[12]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ የእስራኤል ቤት ሽማግሌዎች እያንዳንዳቸው በጣዖታቸው ምስል ጓዳ ውስጥ በጨለማ የሚያደርጉትን አይተሃልን? እነርሱ፣ 'እግዚአብሔር አያየንም፤ እግዚአብሔር ምድሪቱን ትቶአል' ይላሉ" አለኝ። [13]ደግሞም፣ "ከእነዚህ የባሰ አስጸያፊ ነገር ሲሠሩ ታያለህ" አለኝ።

[14]ከዚህም በኋላ በሰሜን በኩል ወዳለው ወደ እግዚአብሔር ቤት በር መግቢያ አመጣኝ፤ በዚያም ሴቶች ተቀምጠው ተሙዝ ለተባለው ጣዖት ሲያለቅሱ አየሁ። [15]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ይህን አይተሃልን? ከዚህም የባሰ አስጸያፊ ነገር ታያለህ" አለኝ።

[16]ደግሞም ወደ እግዚአብሔር ቤት ወደ ውስጠኛው አደባባይ አመጣኝ፤ እነሆም በመተላለፊያውና በመሠዊያው መካከል በቤተ መቅደሱ መግቢያ ላይ ሃያ አምስት ሰዎች ያህል ነበሩ፤ ጀርባቸውን ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፣ ፊታቸውን ወደ ምሥራቅ አድርገው ለምትወጣዋ ፀሓይ ይሰግዱ ነበር።

[17]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ይህን አይተሃልን? የይሁዳ ቤት በዚህ ቦታ የሚፈጽሙት ጸያፍ ተግባር ቀላል ነገር ነውን? ምድሪቱንስ በዐመፅ በመሙላት ዘወትር ያስቈጡኝ ዘንድ ይገባልን? እነሆ፤ ቅርንጫፉን ወደ አፍንጫቸው አቅርበዋል! [18]ስለዚህ በቍጣ እመጣባቸዋለሁ፤ በርኅራኄ ዐይን አላያቸውም፤ ከሚመጣባቸው ነገር አላድናቸውም፤ ወደ ጆሮዬም ቢጮኹ አልሰማቸውም።"

8፥3 ቍ5፡16፤ ዘፀ20፥5፤24፥10፤ ዘዳ32፥16፤ሕዝ2፥9፤ 3፥12፤11፥1
8፥4 ዘፀ24፥16፤ ሕዝ3፥22
8፥5 መዝ78፥58፤ ኤር4፥1፤32፥34
8፥6 መዝ78፥60፤ ሕዝ5፥11፤ሆሴ 5፥6
8፥10 ዘፀ20፥4፤ዘዳ 4፥15-18፤መሳ17፥4 -5፤ኤር16፥18፤44፥4 ፤ሕዝ11፥12፤23፥14
8፥11 ዘፀ3፥16፤ ዘሌ10፥1፤ዘኍ16፥17፡ 35፤ኤር44፥5፤ ሕዝ11፥1-2
8፥12 2ነገ21፥16፤ ኢዮ22፥13፤መዝ 10፥11፤ኢሳ29፥15 ፤ሕዝ9፥9፤ሶፎ1፥12
8፥14 ሕዝ11፥12
8፥16 ቍ3፤ ዘፍ1፥16፤ዘዳ4፥19፤ 17፥3፤ኢዮ31፥28፤ ኤር2፥27፤ሕዝ9፥6፤ 11፥1፡12፤40፥6፤ 43፥1
8፥17 ዘፍ6፥11፤ ዘኍ11፥33፤1ነገ14፥9፤ ሕዝ16፥2፡26
8፥18 1ሳሙ8፥18፤ ኢሳ58፥4፤ ኤር11፥11፤13፥14፤ 44፥6፤ሕዝ5፥11፤ 9፥10፤ 24፥14
9፥2 ዘሌ16፥4፤ ሕዝ10፥2፤ዳን10፥5፤ 12፥6፤ራእ15፥6
9፥3 1ሳሙ4፥21፤ ሕዝ10፥4፤ሕዝ 11፥22

## የጣዖት አምላኪዎች መገደል

**9** ከዚያም እኔ እየሰማሁ ከፍ ባለ ድምፅ፣ "እያንዳንዳቸው በእጃቸው የጦር መሣሪያ የያዙ፣ ከተማዪቱን የሚቀጡ ወደዚህ ይምጡ" ብሎ ከፍ ባለ ድምፅ ጮኸ። [2]እነሆም፤ አጥፊ የሆነ የጦር መሣሪያ በእጃቸው የያዙ ስድስት ሰዎች በሰሜን አቅጣጫ ካለው ከላይኛው በር መጡ፤ ከእነርሱም ጋር ቀጭን በፍታ የለበሰ፣ በጐኑም የጽሕፈት ዕቃ ማኅደር ያነገበ ሰው ነበር። እነርሱም ገብተው በናሱ መሠዊያ አጠገብ ቆሙ።

[3]በዚህ ጊዜ የእስራኤል አምላክ ክብር ከነበረበት ከኪሩብ በላይ ተነሥቶ ወደ ቤተ መቅደሱ መድረክ ሄደ። እግዚአብሔርም በፍታ

---

በዐይን ሙሉ ለማየት የማይቻለውን የመለኮትን መልእክተኛ የሚያመለክት ነው (ማቴ28፥3 ይመ፤ ከሐሥ9፥3 ጋር ያነጻጽሩ)።

8፥3 *ቅናት የሚያነሣሣው ጣዖት፤* በእግዚአብሔር በቤተ መቅደስ ውስጥ የሚቀመጥ ማንኛውም ጣዖት የእግዚአብሔርን ቅናት ያነሣሳል፤ ይህ ጣዖት የልምላሜ አምላክ የምትባለው ከነዓናውያን የሚያመልኳት የአሼራ ምስል ሳይሆን አይቀርም፤ ይህንንም ምስል ኢዮስያስ ከሠላሳ ዓመት በፊት አስወግዶት ነበር (2ነገ23፥6 ይመ)። *ወደ ኢየሩሳሌም ... ወሰደኝ፤* ሕዝቅኤል አስፈሪውን የፍርድ ትንቢት ይናገር ዘንድ ወደ ኢየሩሳሌም ሄዶ ነበር (ም1-7)። አሁን ደግሞ፣ በአምላክ ራእይ ወደ ኢየሩሳሌም ተወሰደ (11፥24 ይመ)፤ ፍርድ የሚመጣበትን ምክንያት አየ።

8፥5 *የቅናት ጣዖት፤* የቍ3 ማብ ይመ።

8፥10 *በደረታቸው የሚሳቡ ፍጡራንና የርኩሳን አራዊት ዐይነት ሁሉ፤* ምናልባት ይህ የግብፃውያንን ሁኔታ የሚያመለክት ይሆናል (2ነገ23፥31-35 ይመ)።

8፥11 *ያእዛንያ፤* በ11፥1 ላይ ከተጠቀሰው ሰው ጋር አንድ አይደለም፤ የስሙ ትርጕም ምፀታዊ ሲሆን፣ ይኸውም "እግዚአብሔር ይሰማል" ማለት ነው፣ ምፀቱም በቍ12 ላይ በግልጽ ይታያል።

8፥14 *ተሙዝ፤* የባቢሎናውያን የልምላሜ ጣዖት ሲሆን፣ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የተጠቀሰው እዚህ ስፍራ ብቻ ነው። የኢየሩሳሌም ሴቶችም፣ ይህ ጣዖት ስለሞተ አለቀሱለት፤ የአለቀሱለትም የዓመቱ አዝመራ በቍሙ ጠውልጐ የቀረው እርሱ ስለሞተ ነው ብለው ያስቡ ነበር። አንዳንድ ሰዎች በዳን11፥37 የተጠቀሰው አምላክ፣ ይህ ጣዖት ሳይሆን አይቀርም ብለው ይናገራሉ።

8፥16 *ጀርባቸውን ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፤ ... አድርገው፤* በአብዛኛው በጥንት የነበሩ ቤተ መቅደሶች ፊታቸው ወደ ምሥራቅ አቅጣጫ የዞረ ነበር። ፀሓይ በምትወጣበት ጊዜ ሊሰግዱላት ከፈለጉም ጀርባቸውን ወደ ቤተ መቅደሱ ማዞራቸው ግድ ነው።

8፥17 *ቅርንጫፉን ወደ አፍንጫቸው አቅርበዋል፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በሌላ ቦታ ያልተገለፀ አባባል ነው፤ ይሁን እንጂ ሰዎች ተፈጥሮን ለማምለክ የሚያደርጉትን ሥርዐታዊ የሰውነት እንቅስቃሴ የሚያመለክት ነው።

9፥1 *ከፍ ባለ ድምፅ፤* እንደ ነጐድጓድ የሚያስገመግም የእግዚአብሔር ድምፅ ማለት ነው (ዘፀ19፥19 እና አግራጌ ትርጕሙን ይመ፤ እንዲሁም መዝ29 ይመ)።

9፥2 *ስድስት ሰዎች ... ከላይኛው በር መጡ፤* እነዚህ ከተማዪቱን የሚጠብቁ ስድስቱ መላእክትና በተጨማሪም የሐር ልብስ የለበሰው ሰባተኛው ሰው (በራእ8፥2፡6 ላይ ከተጠቀሱት ከሰባቱ የፍርድ መላእክት ጋር ያነጻጽሩ) የመጡት ቅናት ያነሣሣው ጣዖት ከቆመበት ስፍራ ነው (የ8፥3 እና ማብ ይመ)። *አጥፊ የሆነ የጦር መሣሪያ፤* ምናልባት ዱላ ወይም መጥረቢያ ይሆናል።

9፥3 *ክብር ... ተነሥቶ ... ሄደ፤* እግዚአብሔር ቤተ መቅደሱን ትቶ ለመሄድ ሲነሣ ክብሩም ወደ በሩ መንቀሳቀሱን

የለበሰውን በጐኑም የጽሕፈት ዕቃ ማኅደር ያነገበውን ሰው ጠራ፤ 4እግዚአብሔርም፣ "በኢየሩሳሌም ከተማ ሁሉ ሂድና በውስጧ ስለ ተሠራው ጸያፍ ተግባር ሲያዝኑና ሲያለቅሱ በነበሩ ሰዎች ግምባር ላይ ምልክት አድርግ" አለው::

5እኔም እየሰማሁ፣ ለሌሎቹ እንዲህ አለ፤ "በከተማዋ ሁሉ እርሱን ተከትላችሁ ግደሉ፤ አዘኔታና ርኅራኄ አታሳዩ፤ ግደሉ፤ 6ሽማግሌውን፣ ጎልማሳውንና ልጃገረዲቱን፣ ሴቶችንና ሕፃናትን ፈጽማችሁ አጥፉ፤ ነገር ግን ምልክቱ ያለበትን ሰው አትንኩ፤ ከቤተ መቅደሴም ጀምሩ::" ስለዚህ በቤተ መቅደሱ ፊት ለፊት ከነበሩት ሽማግሌዎች ጀመሩ::

7እርሱም፣ "ቤተ መቅደሴን አርክሱ፤ አደባባዩንም ሬሳ በሬሳ አድርጉ፤ ሂዱ!" አላቸው:: እነርሱም ወጥተው በከተማዪቱ ሁሉ እየተዘዋወሩ መግደል ጀመሩ:: 8እነርሱ እየገደሉ እኔም ብቻዬን ሳለሁ፣ በግንባሬ ተደፍቼ፣ "ወዮ! ልዑል *እግዚአብሔር* ሆይ፤ በኢየሩሳሌም ላይ መዓትህን አውርደህ የእስራኤልን ትሩፋን ሁሉ ልታጠፋ ነውን?" በማለት ጮኽሁ::

9እርሱም እንዲህ ሲል መለሰልኝ፤ "የእስራኤልና የይሁዳ ቤት ኀጢአት እጅግ በዝቶአል፤ ምድሪቱ በደም ተጥለቅልቃለች፤ ከተማዪቱም ግፍን ተሞልታለች:: እነርሱ፣ '*እግዚአብሔር* ምድሪቱን ትቶአታል፤ *እግዚአብሔር* አያይም' ይላሉ፤ 10እኔም የሠሩትን ሥራ በራሳቸው ላይ እመልስባቸዋለሁ እንጂ፣ በርኅራኄ ዐይን አላያቸውም፤ ከሚመጣባቸውም ነገር አላድናቸውም::"

11እነሆ በፍታ የለበሰውና በጐኑም የጽሕፈት ዕቃ ማኅደር ያነገበው ሰው ተመልሶ፣ "እንዳዘዝኸው ፈጽሜአለሁ" አለ::

## የእግዚአብሔር ክብር ከቤተ መቅደሱ ተለየ

**10** እኔም አየሁ፤ እነሆ ከኪሩቤል ራስ በላይ ካለው ጠፈር ከፍ ብሎ፣ የሰንፔር ዙፋን[ገ] የሚመስል ነገር ነበረ:: 2*እግዚአብሔርም* በፍታ የለበሰውን ሰው፣ "በኪሩቤል ሥር ወዳሉት መንኰራኵሮች መካከል ግባ፤ በኪሩቤል መካከል ካለውም የእሳት ፍም እጅህን ሞልተህ ዝገን፤ በከተማዪቱም ላይ በትነው" አለው:: ሰውዬውም እያየሁት ገባ::

3ሰውዬው ወደ ውስጥ በገባ ጊዜ፣ ኪሩቤል በቤተ መቅደሱ ውስጥ በደቡብ በኩል ቆመው ነበር፤ ደመናም ውስጠኛውን አደባባይ ሞላ:: 4*የእግዚአብሔርም* ክብር ከነበረበት ከኪሩቤል በላይ ተነሥቶ ወደ ቤተ መቅደሱ መድረክ ሄደ፤ ደመናው ቤተ መቅደሱን ሞላ፤ አደባባዩም *በእግዚአብሔር* ክብር ብርሃን ተሞላ:: 5ሁሉን የሚገዛ[ኣ] ስምሳክ ሲናገር እንደሚሰማው ድምፅ ዐይነት፣ የኪሩቤል ክንፎች ድምፅ እስከ ውጪው አደባባይ ድረስ ይሰማ ነበር::

6*እግዚአብሔር* በፍታ የለበሰውን ሰው፣ "ከኪሩቤል ዘንድ ከመንኰራኵሮቹ መካከል እሳት ውሰድ" ብሎ ባዘዘው ጊዜ፣ ሰውዬው ወደ ውስጥ ገብቶ በአንዱ መንኰራኵር አጠገብ ቆመ:: 7ከኪሩቤልም አንዱ በመካከላቸው ወዳለው እሳት እጁን ዘርግቶ ጥቂት ወሰደ፤ በፍታ በለበሰው ሰው እጅ ላይ አኖረው፤ እርሱም ይዞ ወጣ:: 8ከኪሩቤል ክንፎች ሥር የሰው እጅ የሚመስል ይታይ ነበር::

9እኔም አየሁ፤ እነሆ፤ በኪሩቤል አጠገብ አራት መንኰራኵሮች ነበሩ፤ በእያንዳንዱ ኪሩብ አጠገብ አንድ መንኰራኵር ነበር፤ የመንኰራኵሮቹም መልክ እንደ ቢረሌ ያንጸባርቅ ነበር:: 10የአራቱም መልክ ይመሳሰል ነበር፤ እያንዳንዱም መንኰራኵር በመንኰራኵር ውስጥ ተሰክቶ የተሠራ ይመስል ነበር:: 11መንኰራኵሮቹ በሚንቀሳቀሱበት ጊዜም ኪሩቤል ወደ ዞሩበት ወደ አራቱ አቅጣጫ ሁሉ መሄድ ይችሉ ነበር፤ ኪሩቤል በሚሄዱበት ጊዜ መንኰራኵሮቹ ወዲያ ወዲህ[ከ] አይሉም ነበር፤ ኪሩቤል በሚሄዱበት ጊዜ ወዲያ ወዲህ ሳይሉ፣ ራስ ወደ ዞረበት ወደ ማንኛውም አቅጣጫ ይጓዙ ነበር:: 12ጀርባቸውን፣ እጃቸውን፣ ክንፋቸውን ጨምሮ መላ ሰውነታቸው እንዲሁም አራቱ መንኰራኵሮቻቸው በጠቅላላ በዐይን የተሞሉ ነበሩ:: 13መንኰራኵሮቹም፣ "ተሽከርካሪ መንኰራኵሮች" ተብለው ሲጠሩ ሰማሁ:: 14እያንዳንዱም ኪሩብ አራት አራት ፊት ነበሩት፤ ይኸውም አንደኛው ፊት የኪሩብ፣ ሁለተኛው የሰው ፊት፣

[ገ]1 *ወይም ላፒስላዙሊ*
[ኣ]5 *ዕብራይስጡ ሔል-ሻዳይ ይለዋል*
[ከ]11 *ወይም ወደ አንድ ወገን አይሉም ነበር*

9+4 ዘፍ4+15፤ ዘፀ12+7፤ መዝ119+53:136፤ ኤር7+29፤13+17፤ 25+29፤ሕዝ21+6፤ አሞ6+6፤2ቆሮ1+22፤ ራእ7+3
9+5 ዘፀ32+27፤ ኢሳ13+18፤ኤር13+14፤ ሕዝ5+11
9+6 ዘፍ4+15፤ ዘፀ12+7፤ 2ዜና36+17፤ ኤር7+32፤16+6፤ 25+29፤ሕዝ6+4፤ 8+11-13:16፤ 1ጴጥ4+17
9+7 ሕዝ6+7
9+8 ኢያ7+6፤ ሕዝ4+14፤7+8፤ 11+13፤አሞ7+1-6
9+9 ኢዮ22+13፤ መዝ58+2፤ኤር12+1፤ ሕዝ8+12፤14+23፤ 22+29፤ዕን1+4
9+10 ኢሳ22+5፤ 65+6፤ኤር13+14፤ ሕዝ8+18፤11+21፤ 23+49
10+1 ዘፍ3+24፤ ዘፀ24+10፤ሕዝ1+22፤ ራእ4+2
10+2 2ሳሙ22+9፤ ሕዝ1+15፤9+2፤ ራእ8+5
10+4 ዘፀ24+16፤ ሕዝ9+3፤44+4
10+5 ኢዮ40+9፤ ሕዝ3+13
10+6 ዳን7+9
10+7 ሕዝ5+4
10+8 ሕዝ1+8
10+9 ዘፀ28+20፤ ራእ21+20
10+12 ሕዝ1+15 -21፤ራእ4+6-8
10+14 1ነገ7+29: 36፤ሕዝ1+6:10፤ 41+19፤ራእ4+7

ያመለክታል (የ8+1-11+25 ማብ ይመ)::

9+4 *ሲያዝኑና ሲያለቅሱ፤* የተረፉትን ማለት ነው (ዘፀ 12+23፤ 1ነገ19+18 ይመ):: *ምልክት፣* ይህ ምልክት የዕብራይስጥ ፊደል የመጨረሻው ሆሄ የሆነው "ታው" ነው፤ በመጀመሪያ፣ "X" ይመስል ነበር (ከራእ7+2-4፤ 13+16፤ 14+9:11፤ 20+4፤ 22+4 ጋር ያነጻጽሩ)::

9+6 *ከቤተ መቅደሴም ጀምሩ፤* ፍርዱ በእግዚአብሔር ሕዝብ ላይ ይጀምራል ማለት ነው (1ጴጥ4+17 ይመ)::

9+8 *ወዮ! ልዑል እግዚአብሔር ሆይ፤* ነቢዩ ሕዝቅኤል፣ እግዚአብሔር ለምን እንዲህ አደረግህ ብሎ ከጠየቀበት ከጥቂቶቹ ጊዜያት አንዱ ይህ ነው (4+14፤ 11+13 ይመ)::

10+1 *እኔም አየሁ፤* ምዕራፍ ዐሥር ምዕራፍ አንድን ያስተጋባል፤ ሕዝቅኤል፣ በኮቦር ወንዝ ያየውን ራእይ እዚህም ደግሞ አየው (8+4 ይመ):: በምዕራፍ አንድ ላይ ያያቸው ፍጡራን ኪሩቤል ተብለዋል (የ1+5 ማብ ይመ)::

10+2 *የእሳት ፍም፤* በ1+13 ላይ የተጠቀሱት ሕያዋን ፍጡራን የእሳት ፍም ይመስላሉ፤ እዚህ ቦታ ላይ ደግሞ፣ እውነተኛ የእሳት ፍም ናቸው:: *በከተማዪቱም ላይ በትነው፤* በእሳት የሚፈጸመውን ፍርድ ያመለክታል (ዘፍ19+24፤ አሞ7+4 ይመ)::

10+7 *ከኪሩቤልም አንዱ ...እጁን ዘርግቶ፤* "ቀጭን የሐር ልብስ የለበሰው ሰው" የእሳቱን ፍም ራሱ እንዲወስድ በመጀመሪያ ቢታዘዝም (ቍ2)፣ እዚህ ላይ ግን፣ ከፍጡራኑ መካከል ከአንዱ እጅ ተቀበለ (1+8 ይመ):: *እርሱም ይዞ ወጣ፤* ከዚህ በኋላ የተገለጸ ተጨማሪ ነገር ባይኖርም፤ የሚያጠፋው እሳት ግን በኢየሩሳሌም ላይ የተበተነ ይመስላል::

10+14 *አንደኛው ፊት የኪሩብ፤* በ1+10 ላይ የሰው፣ የአንበሳና የንስር ፊት የተባለው፣ እዚህ ካለው ጋር ፍጹም አንድ

ሦስተኛው የአንበሳ ፊት፣ አራተኛውም የንስር ፊት ነበር።

[15]ኪሩቤልም ወደ ላይ ተነሡ፤ እነዚህም በኮቦር ወንዝ አጠገብ ያየኋቸው ሕያዋን ፍጡራን ነበሩ። [16]ኪሩቤል ሲንቀሳቀሱ፣ መንኰራኵሮቹም ከጐናቸው ይንቀሳቀሱ ነበር፤ ኪሩቤልም ከምድር ለመነሣት ክንፋቸውን ሲዘረጉ፣ መንኰራኵሮቹ ከአጠገባቸው አይለዩም ነበር። [17]ኪሩቤል ቀጥ ብለው በሚቆሙበት ጊዜ እነርሱም ደግሞ ይቆማሉ፤ ኪሩቤል ከምድር ከፍ ከፍ በሚሉበት ጊዜ፣ የሕያዋኑ ፍጡራን መንፈስ በውስጣቸው ስላለ፣ መንኰራኵሮችም አብረዋቸው ይነሡ ነበር።

[18]ከዚህ በኋላ፣ *የእግዚአብሔር* ክብር ከቤተ መቅደሱ ደጃፍ ላይ ተነሥቶ ከኪሩቤል በላይ ቆመ። [19]ኪሩቤልም እኔ እያየኋቸው ክንፎቻቸውን ዘርግተው ከምድር ተነሥተው ሄዱ፤ መንኰራኵሮቹም አብረዋቸው ሄዱ፤ *በእግዚአብሔርም* ቤት በምሥራቅ በር መግቢያ ላይ ቆሙ፤ የእስራኤልም አምላክ ክብር በላያቸው ላይ ነበር።

[20]እነዚህ በኮቦር ወንዝ አጠገብ ከእስራኤል አምላክ በታች ያየኋቸው ሕያዋን ፍጡራን ነበሩ፤ ኪሩቤልም እንደሆኑ አስተዋልሁ። [21]እያንዳንዳቸው አራት አራት ፊት፣ አራት አራት ክንፍ፣ ከክንፎቻቸውም ሥር የሰውን እጅ የሚመስል ነበራቸው። [22]ፊታቸውም በኮቦር ወንዝ አጠገብ ካየኋቸው ጋር ይመሳሰል ነበር፤ እያንዳንዱም ቀጥ ብሎ ወደ ፊት ይሄድ ነበር።

## በእስራኤል መሪዎች ላይ የተላለፈ ፍርድ

**11** መንፈስም ወደ ላይ አነሣኝ፤ ከዚያም በምሥራቅ በኩል ወዳለው ወደ *እግዚአብሔር* ቤት በር አመጣኝ። በበሩም መግቢያ ላይ ሃያ አምስት ሰዎች ነበሩ፤ በእነርሱም መካከል የሕዝቡን መሪዎች የዓዙርን ልጅ ያእዛንያንና የበናያስን ልጅ ፈላጥያንን አየሁ። [2]*እግዚአብሔርም* እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ እነዚህ ሰዎች ክፋትን የሚያቅዱና በዚህችም ከተማ ላይ ተንኰልን የሚመክሩ ናቸው። [3]እነርሱም፣ 'ቤቶች የሚሠሩበት ጊዜ ቅርብ አይደለምን?[a] ይህች ከተማ ድስት ናት፤ እኛም ሥጋ ነን' ብለዋል። [4]ስለዚህ ትንቢት ተናገርባቸው፤ የሰው ልጅ ሆይ፤ ትንቢት ተናገር።"

10፥15 መዝ137፥1፤ ኢሳ6፥2
10፥17 ሕዝ3፥13
10፥18 1ሳሙ4፥21፤ መዝ18፥10
10፥19 ሕዝ11፥1፤ 22፤43፥4
10፥20 ሕዝ1፥1
10፥21 ሕዝ1፥6፤ 41፥18
10፥22 ሕዝ1፥1
11፥1 ቍ13፤ ኤር5፥5፤ሕዝ8፥16፤ 10፥19፤43፥4-5
11፥2 ኢሳ29፥20 ፤ሕዝ8፥11፤ናሆ1፥11
11፥3 ቍ7፤ ኤር1፥13፤ሕዝ12፥22፤ 27፤24፥3፤ሚክ3፥3
11፥4 ሕዝ3፥4፡17
11፥5 መዝ26፥2፤ ኤር17፥10
11፥6 ሕዝ7፥23፤ 22፥6
11፥7 ቍ3፤ ኤር1፥13፤ ሕዝ24፥3-13፤ ሚክ3፥2-3
11፥8 ዘሌ26፥25፤ ምሳ10፥24፤ ኢሳ66፥4፤ኤር42፥16
11፥9 ዘዳ28፥36፤ መዝ106፥41፤ ሕዝ 5፥8
11፥10 2ነገ14፥25
11፥11 ቍ3፤ ሕዝ24፥6
11፥12 ዘሌ18፥4፤ ሕዝ6፥7፤18፥10፤ 18፥9
11፥13 ቍ1፤ ሕዝ9፥8፤አሞ7፥2
11፥15 ሕዝ33፥24
11፥16 መዝ31፥20፤ 90፥1፤91፥9፤ ኢሳ 4፥6

[5]*የእግዚአብሔርም* መንፈስ በላዬ ወረደ፤ እንዲህም አለኝ፤ "*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'የእስራኤል ቤት ሆይ፤ እናንተ እንዲህ ብላችኋል፤ እኔ ግን የልባችሁን ሐሳብ ዐውቃለሁ። [6]በዚህች ከተማ ብዙ ሰው ገድላችኋል፤ መንገዶቿንም ሬሳ በሬሳ አድርጋችኋል።'

[7]"ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'በዚያ የጣላችኋቸው ሬሳዎች እነርሱ ሥጋ ናቸው፤ ይህችም ከተማ ድስት ናት፤ እናንተን ግን ከውስጧ አወጣችኋለሁ። [8]ሰይፍን ፈርታችኋል፤ እኔም ሰይፍ እልክባችኋለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*። [9]ከከተማዪቱ አውጥቼ ለባዕዳን አሳልፌ እሰጣችኋለሁ፤ ፍርድንም አመጣባችኋለሁ። [10]በሰይፍ ትወድቃላችሁ፤ በእስራኤል ድንበር ላይ እፈርድባችኋለሁ፤ በዚያ ጊዜም እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ። [11]ይህች ከተማ ድስት አትሆንላችሁም፤ እናንተም በውስጧ ሥጋ አትሆኑም፤ በእስራኤልም ድንበር ላይ እፈርድባችኋለሁ፤ [12]በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ፤ እናንተ በዙሪያችሁ ያሉትን አሕዛብ ሥርዐት ተከተላችሁ እንጂ ትእዛዜን አልፈጸማችሁም ሕጌንም አልጠበቃችሁምና።"

[13]ትንቢት እየተናገርሁ ሳለ፣ የበናያስ ልጅ ፈላጥያ ሞተ፤ እኔም በግንባሬ ተደፍቼ፣ "ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፣ ወዮ! የእስራኤልን ቅሬታ ፈጽመህ ታጠፋለህን?" በማለት በታላቅ ድምፅ ጮኽሁ።

[14]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [15]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ወንድሞችህ፣ የራስህ ዘመዶችና[b] የእስራኤል ቤት ሁሉ፤ '*ከእግዚአብሔር* ርቀዋል፤ ይህች ምድር ርስት ሆና ለኛ ተሰጥታናለች' ብለው የኢየሩሳሌም ነዋሪዎች የተናገሩባቸው ናቸው።[c]

## የእስራኤል የመመለስ ተስፋ

[16]"ስለዚህ እንዲህ በል፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "በአሕዛብ መካከል ብሰድዳቸውም፣ በአገሮች መካከል ብበትናቸውም፣ በሄዱባቸው አገሮች ሁሉ ለጥቂት ጊዜ መቅደስ ሆኜአቸዋለሁ' "።

[a]3 *ወይም ቤቶችን ለመሥራት ጊዜው አሁን አይደለም*
[b]15 *ወይም በምርኮ ከአንተ ጋር የነበሩና* (ሰብዐ ሊቃናትና ሱርስትን ይመ)
[c]15 *ወይም የኢየሩሳሌም ሰዎች የተናገሩባቸው፣ 'ከእግዚአብሔር ራቁ'*

ሆኖ ሳለ፣ እዚያ "የበሬ ፊት" የነበረው ግን እዚህ ላይ፣ "የኪሩብ ፊት" ተብሎአል (የዘፍ3፥24 ማብ ይመ)።

10፥19 *በምሥራቅ በር ... የእስራኤልም አምላክ ክብር በላያቸው ላይ ነበር፤* የእግዚአብሔር ክብር፣ ለሁለተኛ ጊዜ እንደ ገና ወደ ምሥራቅ አቅጣጫ ተንቀሳቀሰ (ቍ4፤ 9፥3፤ እንዲሁም የ8፥1-11፥25 ማብ ይመ)።

11፥1 *ያእዛንያ፤* የ8፥11 ማብ ይመ። *ፈላጥያ፤* "እግዚአብሔር ይታደጋል" ማለት ነው።

11፥3 *ቤቶች የሚሰሩበት ጊዜ ቅርብ አይደለምን?* በ597 ዓ.ቅ.ክ. ላይ በምርኮ ያልሄዱት የኢየሩሳሌም ነዋሪዎች፣ የከፋ ነገር እንደማይገጥማቸው በማሰብ ተዝናንተው ተቀመጡ። *ድስት፤* በም24 እንደተገለጸው ኢየሩሳሌም ከምግብ ማብሰያ ድስት ጋር ተነጻጽራለች፣ ሳይማረኩ የቀሩት በምርኮ ወደ ባቢሎን የተወሰዱትን እንደተጣለ ዐጥንት በመቍጠር (ቍ15 ይመ) ራሳቸውን እንደ ምርጥ፣ "ሥጋ" አዩት።

11፥7 *በዚያ የጣላችኋቸው ሬሳዎች እነርሱ ሥጋ ናቸው፤* በትንቢተ ኤርምያስ፣ "ሥጋ" ተብሎ የተገለጸው፣ በኢየሩሳሌም በሥልጣን ላይ ያሉትንና ተማርከው የተወሰዱትን ሲሆን፣ እዚህ ላይ ግን፣ እነዚህ ባለሥልጣናት የገደሉአቸውን ንጹሐን ሰዎችን ነው።

11፥11 *በእስራኤልም ድንበር ላይ፤* በሪብላ ማለት ነው (2ነገ25፥20-21 ይመ)።

11፥13 *ልዑል እግዚአብሔር ወዮ!* የ9፥8 ማብ ይመ።

11፥16 *መቅደስ ሆኜአቸዋለሁ፤* በትንቢተ ሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ይህ ቍጥር መሪ ሐሳብን የያዘ ነው፤ እግዚአብሔር

17 “ስለዚህ እንዲህ በል፤ ‘ልዑል *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ከአሕዛብ መካከል እሰበስባችኋለሁ፤ ከተበተናችሁባቸው አገሮች እመልሳችኋለሁ፤ የእስራኤልንም ምድር እንደ ገና እሰጣችኋለሁ።”

18 “ወደዚያ በተመለሱ ጊዜ የረከሱ ምስሎቿንና ጸያፍ ተግባሯን ያስወግዳሉ። 19 የማያወላውል ልብ እሰጣቸዋለሁ፤ አዲስ መንፈስ በውስጣቸው አኖራለሁ፤ ድንጋዩን ልብ ከውስጣቸው አወጣለሁ፤ ሥጋ ልብም እሰጣቸዋለሁ። 20 ስለዚህ ትእዛዜን ይፈጽማሉ፤ ሕጌን ይጠብቃሉ። እነርሱ ሕዝቤ ይሆናሉ፤ እኔም አምላካቸው እሆናለሁ። 21 ነገር ግን ልባቸው ወደ ረከሱ ምስሎቻቸውና ወደ ጸያፍ ተግባራቸው ያዘነበለውን እንደ ሥራቸው እከፍላቸዋለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*።”

22 ኪሩቤልም ክንፎቻቸውን ዘረጉ፤ መንኰራኵሮቹም በአጠገባቸው ነበሩ፤ የእስራኤልም አምላክ ክብር በላያቸው ላይ ነበር። 23 የ*እግዚአብሔርም* ክብር ከከተማዪቱ ውስጥ ተነሥቶ ወጣ፤ ከከተማዪቱም በስተ ምሥራቅ ካለው ተራራ በላይ ቆም አለ። 24 መንፈስም ወደ ላይ አነሣኝ፤ በእግዚአብሔርም መንፈስ በተሰጠው ራእይም በባቢሎን[a] ምድር ወደ ነበሩት ምርኮኞች አመጣኝ።

ከዚያም ያየሁት ራእይ ከእኔ ወጥቶ ሄደ፤ 25 እኔም *እግዚአብሔር* ያሳየኝን ነገር ሁሉ ለምርኮኞቹ ተናገርሁ።

## ምርኮው በትእምርት መቅረቡ

**12** የ*እግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 2 “የሰው ልጅ ሆይ፤ በዐመፀኛ ሕዝብ መካከል ተቀምጠሃል፤ የሚያዩበት ዐይን አላቸው፤ ነገር ግን አያዩም፤ የሚሰሙበትም ጆሮ አላቸው፤ ነገር ግን አይሰሙም፤ ዐመፀኛ ሕዝብ ናቸውና።

3 “ስለዚህ የሰው ልጅ ሆይ፤ እነርሱ እያዩህ በቀን ጓዝህን ጠቅልለህ ለመሰደድ ተዘጋጅ፤ ካለህበትም ስፍራ ተነሥተህ ወደ ሌላ ቦታ ሂድ፤ ዐመፀኛ ቤት ቢሆኑም ምናልባት ይህን ያስተውሉታል። 4 በቀን እያዩ ጓዝህን እንደ ስደተኛ ጓዝ አውጣው፤ በምሽትም እያዩህ ስደተኛ እንደሚወጣ ውጣ። 5 እነርሱ እያዩ ግንቡን ነድለህ ጓዝህን በዚያ አሹልክ። 6 በፊታቸው ጓዝህን በትከሻህ ላይ አስቀምጥ፣ በምሽትም ተሸክመህ ውጣ። ለእስራኤል ቤት ምልክት አድርጌሃለሁና ምድሪቱን እንዳታይ ፊትህን ሸፍን።”

7 እኔም በታዘዝሁት መሠረት አደረግሁ፤ በቀን ጓዜን ጠቅልዬ እንደ ስደተኛ ጓዝ አወጣሁ፤ በምሽትም ግንቡን በእጄ ነደልሁት፤ እያዩኝም በምሽት ጓዜን በትከሻዬ ላይ ተሸክሜ አወጣሁ።

8 በማግስቱም ጠዋት የ*እግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 9 “የሰው ልጅ ሆይ፤ ዐመፀኛው የእስራኤል ቤት፣ ‘ይህ የምታደርገው ምንድን ነው?’ ብለው ጠይቀውህ አልነበረምን?”

10 “እንዲህ በላቸው፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ይህ የትንቢት ቃል በኢየሩሳሌም ለሚኖረው መስፍንና በዚያ ለሚገኙት ለእስራኤል ቤት ሁሉ ነው” ’። 11 ‘እኔ ምልክታችሁ ነኝ’ በላቸው።

“እኔ እንዳደረግሁት፤ እንዲሁ በእነርሱ ይደረግባቸዋል፤ በምርኮኛነትም ተሰደው ይሄዳሉ።

12 “በመካከላቸው ያለው መስፍን በምሽት ጓዙን በትከሻው ተሸክሞ ይወጣል፤ ሾልኮ እንዲሄድ ግንቡ ይነደልለታል፤ ምድሪቱንም እንዳያይ ፊቱን ይሸፍናል። 13 መረቤን በእርሱ ላይ እዘረጋለሁ፤ በወጥመዴም ይያዛል፤ ወደ ከለዳውያን ምድር ወደ ባቢሎን አመጣዋለሁ፤ ነገር ግን እርሷን ሳያያት በዚያ ይሞታል። 14 በዙሪያው ያሉትን ረዳቶቹንና

11፥17 ነህ1፥9፤ ኤር3፥18፤24፥5-6፤ 31፥16፤ሕዝ20፥41፤ 28፥25፤34፥13፤ 36፥28
11፥18 ሕዝ5፥11፤ 37፥23
11፥19 ዘዳ30፥12፤ መዝ86፥11፤ ሕዝ18፥31፤ ዘካ7፥12፤ሮሜ2፥5፤ 2ቆሮ3፥3
11፥20 ዘፀ6፥7፤ መዝ1፥2፤ኤር11፥4፤ 32፥38፤ሕዝ14፥11፤ 34፥30፤36፥26-28፤ ሆሴ1፥9፤ዘካ8፥8፤ ዕብ8፥10
11፥21 ኤር16፥11፤ 16፥18፤ሕዝ9፥10፤ 16፥43
11፥22 ዘፀ24፥16፤ ሕዝ9፥3፤10፥19
11፥23 ሕዝ1፥28፤ 10፥4፤ዘካ14፥4
11፥24 ሕዝ37፥1፤ 43፥5፤2ቆሮ12፥2-4
11፥25 ሕዝ3፥4፡11
12፥2 መዝ78፥40፤ ኢሳ6፥10፤ኤር42፥21፤ማቴ13፥15፤ ማር4፥12፤8፥18
12፥3 ቍ11፤ኤር 26፥3፤36፥3፤ሕዝ3፥27፤2ጢሞ2፥25-26
12፥4 ቍ12፤2ነገ 25፥4፤ኤር39፥4
12፥5 ኤር52፥7፤ አሞ4፥3
12፥6 ቍ12፤ኢሳ 8፥18፤20፥3
12፥7 ሕዝ24፥18፤ 37፥10
12፥9 ሕዝ17፥12፤ 20፥49፤24፥19
12፥11 2ነገ25፥7፤ ኢሳ8፥18፤ኤር15፥2፤ 52፥15፤ዘካ3፥8

12፥12 ኤር39፥4፤ 52፥7 12፥13 ኢሳ24፥17-18፤ኤር24፥8፤ 39፥7፤52፥11፤ሰቆ4፥20፤ሕዝ1፥3፤17፥16፡20፤ 19፥8፤32፥3፤ ሆሴ7፥12 12፥14 2ነገ25፥5፤ ኤር21፥7፤ሕዝ5፥10፡ 12፤17፥21

[a] 24 ወይም *ከለዳውያን*

በሕዝቡ መካከል ለመሆኑ ማስረጃ ከሆነው ቤተ መቅደስና ከኢየሩሳሌም እነርሱ ተሰድደው በምርኮ ቢሄዱም፣ እግዚአብሔር ራሱ በሄዱበት ሁሉ መቅደሳቸው ሆኖአል። በኋለኛውም ዘመን ራሱ ክርስቶስ የቤተ መቅደሱ ምትክ ሆኖ ተገኝቶአል (ዮሐ2፥19-21 ይመ)።

11፥19 *የማያወላውል ልብ ... አዲስ መንፈስ፤* አንድ ሰው ራሱን ለጌታ በአንድ ልብ እንዲሰጥና ለፈቃዱም እንዲገዛ የሚያደርግ ከውስጥ የመነጨ መንፈሳዊና ሥነ ምግባራዊ ለውጥን ያመለክታል (36፥26 ይመ)።

11፥20 *እነርሱ ሕዝቤ ይሆናሉ፣ እኔም አምላካቸው እሆናለሁ፤* የእግዚአብሔር ኪዳን ተስፋ ማዕከል ነው (ዘፀ6፥7 ይመ)።

11፥23 *የእግዚአብሔር ክብር ... ተነሥቶ ወጣ፤* እግዚአብሔር ቤተ መቅደሱን ትቶ በሄደ ጊዜ እንደ ሆነው ሁሉ ክብሩ ለመጨረሻ ጊዜ ወደ ምሥራቅ አቅጣጫ ያደረገው እንቅስቃሴና በኋላም በደብረ ዘይት ተራራ ላይ መቆሙን ያመለክታል (9፥3፤ 10፥4፡19 ይመ፤ እንዲሁም የ8፥1-11፡25 ማብ ይመ)።

*11፥24፤* የ8፥3 ማብ ይመ።

12፥2 *የሚያዩበት፣ ዐይን አላቸው፤ ነገር ግን አያዩም፤* ለኢሳይያስ እግዚአብሔር እንደ ተናገረው ዐይነት የልብ ድንዳኔ ማለት ነው (ኢሳ6፥9-10)።

12፥3 *ጓዝህን ጠቅልለህ፤* በም4-5 ላይ እንዳለው ዐይነት ሌላ ትእምርታዊ አቀራረብ ሲሆን፣ ከእዚህ የሚቀጥለው ደግሞ ራእይ ነው። *ምናልባት ይህን ያስተውሉታል፤* ንስሓ ገብተው መንገዳቸውን ለመለወጥ የሚያስችል ጥቂት ተስፋ ነው።

12፥5 *ግንቡን ነድለህ፤* ከድንጋይ የተሠራውንና እጅግ ወፍራም የሆነውን የከተማዪቱን ግንብ ሳይሆን፣ ከጡብ የተሠራውን የቤቱን ግንብ ሊሆን ይችላል።

12፥6 *ምልክት፤* ነቢያት ትእምርታዊ የሆነ ድርጊት እንዲፈጽሙ እንዲያደርጉ ብዙ ጊዜ በእግዚአብሔር ይታዘዙ ነበር (ለምሳሌ ቍ11፤ 24፥24፡27 ይመ)።

12፥8 *ጠዋት፤* የእግዚአብሔር ቃል ወደ ሕዝቅኤል የመጣው የታዘዘውን ካደረገ በኋላ ነው (ቍ7)። መለኮታዊው ገለጻ ለነቢዩ እንደ ደገና የመጣለት ያለአንዳች ጥያቄ እግዚአብሔርን ስለ ታዘዘ ነው (የ8፥3 ማብ ይመ)።

12፥9 *ይህ የምታደርገው ምንድን ነው?* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ነቢዩ በትእምርት ላቀረበው ገለጻ፣ ለመጀመሪያ ጊዜ ሕዝቡ ስላቀረቡለት ጥያቄ በሕዝቅኤል መጽሐፍ የተመለከተበት ነው።

12፥10 *በኢየሩሳሌም ለሚኖረው መስፍን፤* ሴዴቅያስን ነው (የ7፥27 ማብ ይመ)።

12፥13 *እርሷን ሳያያት፤* የናቡከደነፆር ሰዎች፣ የሴዴቅያስን ዐይኖች ያወጣሉ (2ነገ25፥7 ይመ)።

ወታደሮቹን ሁሉ ወደ ነፋስ እበትናቸዋለሁ፤ በተመዘዘም ሰይፍ አሳድዳቸዋለሁ።

[15]“በአሕዛብ መካከል ስበትናቸውና በአገሮችም መካከል ስዘራቸው፣ በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ። [16]ነገር ግን በሄዱባቸው አሕዛብ መካከል ስለ ጸያፍ ተግባራቸው ይናገሩ ዘንድ ከእነርሱ ጥቂቶቹን ከሰይፍ ከራብና ከቸነፈር አተርፋለሁ። በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።”

[17]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [18]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ምግብህን በድንጋጤ ብላ፤ ውሃህንም በፍርሀትና በመንቀጥቀጥ ጠጣ። [19]ለምድሪቱ ሕዝብ እንዲህ በል፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* በኢየሩሳሌምና በእስራኤል ምድር ስለሚኖሩት እንዲህ ይላል፤ “በዚያ ከሚኖሩ ሰዎች ሁሉ ዐመፅ የተነሣ ምድራቸው ስለምትራቈት፣ ምግባቸውን በጭንቀት ይመገባሉ፤ ውሃቸውንም በፍርሀት ይጠጣሉ። [20]ሰው ይኖርባቸው የነበሩ ከተሞች ባድማ ይሆናሉ፤ ምድሪቱም ወና ትሆናለች። በዚያ ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ።’ ”

[21]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [22]“የሰው ልጅ ሆይ፤ በእስራኤል ምድር፣ ‘ዘመኑ ረዝሞአል፤ ራእዩ ሁሉ ከንቱ ሆኖአል’ የምትሉት ይህ አባባል ምንድነው? [23]እንዲህ በላቸው፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ይህን አባባል እሽራለሁ፤ በእስራኤልም ምድር ዳግመኛ በንግግራቸው አይጠቀሙበትም”። እንዲህም በላቸው፤ “ራእዩ ሁሉ የሚፈጸምበት ጊዜ ቀርቦአል፤ [24]በእስራኤል ሕዝብ መካከል ከእንግዲህ ሐሰተኛ ራእይና አሳሳች ሟርት አይገኝምና። [25]ነገር ግን እኔ *እግዚአብሔር* እናገራለሁ፤ የምናገረውም ቃል ሳይዘገይ ይፈጸማል፤ እናንተ ዐመፀኛ ቤት ሆይ፤ የተናገርሁትን ሁሉ በዘመናችሁ እፈጽማለሁ” ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*።’ ”

[26]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [27]“የሰው ልጅ ሆይ፤ የእስራኤል ቤት፣ ‘ይህ ሰው የሚያየው ራእይ ገና ለሩቅ ዘመን የሚሆን ነው፤ የሚናገረውም ትንቢት የረጅም ጊዜ ትንቢት ነው’ ይላሉ።

[28]“ስለዚህ እንዲህ በላቸው፣ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ከተናገርሁት ቃል ከእንግዲህ የሚዘገይ የለም፤ የምለው ሁሉ ይፈጸማል” ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*።’ ”

## የሐሰተኛ ነቢያት መወገዝ

**13** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ትንቢት በሚናገሩት በእስራኤል ነቢያት ላይ ትንቢት ተናገር፤ ከገዛ ራሳቸው ትንቢት የሚናገሩትን እንዲህ በላቸው፤ ‘*የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ፤ [3]ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “አንዳች ነገር ሳያዩ የራሳቸውን መንፈስ ለሚከተሉ ሞኞች[v] ነቢያት ወዮላቸው! [4]እስራኤል ሆይ፤ ነቢያትሽ በፍርስራሽ መካከል እንደሚኖሩ ቀበሮዎች ናቸው። [5]*በእግዚአብሔር* ቀን በሚሆነው ጦርነት ጸንቶ መቆም እንዲችል፣ የተሰነጠቀውን ቅጥር ለእስራኤል ቤት ለመጠገን ወደዚያ አልወጣችሁም። [6]ራእያቸው ሐሰት፣ ትንቢታቸው ውሸት ነው፤ *እግዚአብሔር* ሳይልካቸው፣ ‘*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል’ ይላሉ፤ ይህም ሆኖ የተናገሩት ይፈጸማል ብለው ይጠብቃሉ። [7]እኔ ሳልናገር፣ ‘*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል’ ስትሉ ሐሰተኛ ራእይ ማየታችሁ፣ ውሸተኛስ ትንቢት መናገራችሁ አይደለምን?”

[8]“ ‘ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ቃላችሁ ሐሰት፣ ራእያችሁም ውሸት ስለ ሆነ እኔ በእናንተ ላይ ተነሥቻለሁ፤ ይላል ልዑል *እግዚአብሔር*። [9]እጄ የሐሰት ራእይ በሚያዩና በሚያሟርቱ ነቢያት ላይ ተነሥቶአል። የሕዝቤ ጉባኤ ተካፋይ አይሆኑም፤ በእስራኤል ቤት መዝገብ አይጻፉም፤ ወደ እስራኤልም ምድር አይገቡም። በዚያ ጊዜ እኔ ጌታ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ።

[v]3 ወይም *ክፉዎች*

12+15 ዘሌ26+33
12+16 ኤር22+8-9፤ ሕዝ6+8-10፤14+22፤ 36+20
12+18 ሰቆ5+9
12+19 ኤር10+22፤ ሕዝ4+16፤6+6-14፤ 23+33፤ሚክ7+13፤ ዘካ7+14
12+20 ኢሳ7+23 -24፤ኤር4+7፤25+9
12+22 መዝ49+4፤ ኢሳ5+19፤ሕዝ11+3፤ አሞ6+3፤2ጴጥ3+4
12+23 መዝ37+13፤ ሕዝ7+7፤18+3፤ ኢዩ2+1፤ሶፎ1+14
12+24 ኤር14+14፤ ሕዝ13+23፤ ሚክ3+6፤ዘካ13+2-4
12+25 ዘኍ11+23፤ 14+28-34፤ ኢሳ14+24፤55+11፤ ኤር16+9፤ሕዝ13+6፤ ዕን1+5፤2+3
12+27 ሕዝ11+3፤ ዳን10+14፤ ማቴ24+48-50፤ 2ጴጥ3+4
13+2 ቍ17፤ ኢሳ9+15፤ኤር23+16፤ 28+15፤37+19፤ ሕዝ22+28
13+3 ኤር23+25 -32፤ሰቆ2+14፤ ሆሴ9+7
13+5 ኢሳ58+12፤ ሕዝ7+19፤22+30፤ 30+3
13+6 ኤር5+1፤ 14+14፤23+16፤ 28+15፤29+9፤ ሕዝ12+24-25፤22+28
13+7 ኢሳ30+10
13+8 ኤር21+13
13+9 ዘፀ6+2፤ 32+32፤ዘዳ13+3፤ ኤር17+13፤20+3-6፤ ሕዝ 20+38

12+18 *በድንጋጤ ብላ፤* ሌላ ትንቢታዊ ትእምርት ነው፤ በዕብራይስጥ፣ “ድንጋጤ” የሚለው ቃል ትርጕም የምድር መናወጥ ከሚያደርሰው ሁኔታ ጋር የሚመሳሰል በመሆኑ፣ የቢዩ ሕዝቅኤል ድንጋጤ ከፍተኛ መሆኑን ያመለክታል (አሞ1+1፤ 1ነገ19+11 ይመ)።

12+19 *ለምድሪቱ ሕዝብ፤* የ7+27 ማብ ይመ።

12+22 *አባባል፤* በፌዝ የተነገረ ነው፤ ምናልባትም በሐሰተኞች ነቢያት የተነገረ ሊሆን ይችላል (ም13፤ ኤር23+9-40፤ 28 ይመ)፤ ሕዝቡም ከአፉ የማይለየው የፌዝ አነጋገር ነው። *ራእዩ፤* በዕብራይስጡ የዚህ ቃል ትርጕም፣ በ1+1 ላይ ከተገለጸው ጋር ተመሳሳይ አይደለም፤ ነገር ግን በ7+26 ላይ ከተገለጸው ጋር አንድ ዐይነት ነው። ይህ፣ “ራእይ” መጽፍ ያለበትን መልእክት (ዕን2+2 ይመ) በተለይም ሕዝቅኤል የተናገረውን የፍርድ ትንቢት የሚያመለክት ነው።

12+23 *ራእዩ ሁሉ የሚፈጸምበት፤* ስለ እውነተኛው የትንቢት ቃል የተሰጠ መለኮታዊ ማረጋገጫ ነው (ከኢሳ 55+11 ጋር ያነጻና)።

12+27 *የረጅም ጊዜ፤* የመጀመሪያው ምሳሌ የሕዝቅኤል ትንቢት ከቶ የሚፈጸም አይደለም የሚል ሲሆን፣ ይኸኛው ግን ትንቢቱ የሚፈጸም ቢሆንም እንኳ፣ ከብዙ ዘመን በኋላ ገና ወደ ፊት የሚደርስና ይህንንም ትውልድ አይመለከትም የሚል ነው።

13+2 *ከገዛ ራሳቸው፤* ከኤር23+21-22 ጋር ያነጻጽሩ።

13+3 *አንዳች ነገር ሳያዩ፤* ከእግዚአብሔር ራእይ አላገኙም ማለት ነው።

13+4 *ቀበሮዎች፤* የሞተ እንስሳ ለመብላት ብዙ ሆነው የሚሄዱ አውሬዎች ናቸው፤ ይህ አገላለጽ አሉታዊ ገጽታ ነው (መዝ63+10፤ ሰቆ5+18 ይመ)።

13+5 *በእግዚአብሔር ቀን፤* የ7+7 ማብ ይመ። *አልወጣችሁም፤* እዚህ ላይ የእውነተኞቹ ነቢያት ሥራ ተገልጾአል (ከ22+30፤ መዝ106+23 ጋር ያነጻጽሩ)።

13+6 *ራእያቸው ሐሰት ... ነው፤* ሐሰተኞች ነቢያት፣ እርግጠኛ ራእይ ይኑራቸው ወይም አይኑራቸው አይታወቅም፤ እነርሱ ግን ከእግዚአብሔር ራእይ እንደ ተቀበሉ ይናገራሉ፤ ይሁን እንጂ፣ የመልእክታቸው ይዘት ሲመረመር፣ አድማጮቻቸው ሊሰሙ የሚፈልጉትን ብቻ እንደሆነ ይታወቃል (ኢሳ 30+10፤ ኤር23+9-17፤ 2ጢሞ4+3 ይመ)።

13+8 *እኔ በእናንተ ላይ ተነሥቻለሁ፤* 5+8 እና ማብ ይመ።

13+9 *ተካፋይ አይሆኑም፤* ቅጣቱ በሦስት መንገድ የሚ መጣባቸው ቅጣት ከማኅበረ ሰቡ ፈጽሞ እንዲወገዱ ያደርጋ

10"ሰላም ሳይኖር፣ 'ሰላም አለ' እያሉ ሕዝቤን ያስታሉ፤ ሕዝቡ ካብ ሲሰራ እነርሱ በኖራ ይለስናሉ፤ 11ስለዚህ በኖራ ለሚለስኑት ካቡ እንደሚወድቅ ንገራቸው:: ዶፍ ይወርዳል፤ ታላቅ የበረዶ ድንጋይ እሰዳለሁ፤ ዐውሎ ነፋስም ይነሣል:: 12እነሆ ካቡ ሲፈርስ ሕዝቡ 'የለሰናችሁበት ኖራው ወዴት ሄደ?' ብለው አይጠይቁአችሁምን?"

13" 'ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "በመዓቴ አውሎ ነፋስ እሰዳለሁ፣ በቍጣዬ የበረዶ ድንጋይ እልካለሁ፤ ዶፍም ከታላቅ ጥፋት ጋር ይወርዳል:: 14በኖራ የለሰናችሁትን ካብ አፈርሳለሁ፤ መሠረቱም ተገልጦ እስኪታይ ድረስ ከምድር ጋር አደ ባልቀዋለሁ:: ቅጥሩ[a] በሚወድቅበት ጊዜ፣ እናንተም በውስጡ ታልቃላችሁ:: በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ:: 15መዓቴንም በቅጥሩና ኖራ በለሰኑት ሰዎች ላይ እሰዳለሁ፤ እናንተንም እንዲህ እላችኋለሁ፤ 'ቅጥሩና ቅጥሩን በኖራ የለሰኑት የሉም፤ 16ኢየሩሳሌም ትን ቢት የተናገሩላትና ሰላም ሳይኖር የሰላም ራእይ ያዩላት የእስራኤል ነቢያት ጠፍ ተዋል፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::' "

17"አሁንም የሰው ልጅ ሆይ፤ ከራሳቸው አመንጭተው ትንቢት ወደሚናገሩ ወደ ሕዝብህ ሴቶች ልጆች ፊትህን መልስ፤ ትንቢትም ተናገርባቸው፤ 18እንዲህም በል፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "የሕዝብን ነፍስ ለማጥመድ፣ ለእስማታቸው ለእጃቸው አንጓ ሁሉ አሸንክታብ ለሚያሰፋና፣ የተለያየ መጠን ያለውን የራስ መሸፈኛ ለሚያበጁ ሴቶች ወዮላቸው! በውኑ የሕዝቤን ነፍስ እያጠመዳችሁ የራሳችሁን ነፍስ ታድናላችሁን? 19ዕፍኝ ለማይሞላ ገብስና ለቍራሽ እንጀራ ስትሉ ሐሰትን የሚያደምጥ ሕዝቤን እየዋሻችሁ መሞት የማይገባውን በመግደል፣ መኖር የማይገባውንም በማትረፍ በሕዝቤ መካከል አርክሳችሁኛል::

20" 'ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "እነሆ የሕዝብን ነፍስ እንደ ወፍ በምታጠምዱበት አሸንክታብ ላይ ተነሥቻለሁ፤ ከክንዳችሁ ላይ እቀዳድደዋለሁ፤ እንደ ወፍ የምታጠምዱትንም ሕዝብ ነጻ አወጣዋለሁ:: 21መሸፈኛችሁን ቀድጄ ሕዝቤን ከእጃችሁ አድናለሁ፤ ከእንግዲህም ወዲህ በቍጥጥራችሁ ሥር አይሆኑም፤ በዚያ ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ:: 22እኔ ያላሳዘንሁትን ጻድቅ በውሸት ስላሳዘናችሁ፣ ኀጢአተኛም ከክፉ መንገዱ ተመልሶ ሕይወቱን እንዳያድን በኀጢአቱ ስላበረታታችሁት፣ 23ከእንግዲህ የሐሰት ራእይ አታዩም፣ ሟርትም አታሟርቱም፤ ሕዝቤን ከእጃችሁ አድናለሁ፤ በዚያ ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ::' "

## ባዕድ አምልኮ ተከታዮች መወገዛቸው

**14** ከእስራኤል ሽማግሌዎች አንዳንዶቹ ወደ እኔ መጥተው በፊቴ ተቀመጡ:: 2*የእግዚአብሔርም* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 3"የሰው ልጅ ሆይ፤ እነዚህ ሰዎች ጣዖቶቻቸውን በልባቸው አኑረዋል፤ ክፉታቸውን እንደ ማሰናከያ ድንጋይ በፊታቸው አስቀምጠዋል፤ ታዲያ ከእኔ እንዳች ነገር እንዲጠይቁ ልፈቅድላቸውን? 4ስለዚህ እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ማንኛውም እስራኤላዊ ጣዖትን በልቡ አኑሮ፣ ክፉቱንም የማሰናከያ ድንጋይ አድርጎ በፊቱ በማስቀመጥ ወደ ነቢይ ቢመጣ፣ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ጣዖቱ ብዛት እመልስለታለሁ:: 5በጣዖቶቻቸው ምክንያት ከእኔ የተለዩትን የእስራኤልን ቤት ሁሉ ልብ ወደ ራሴ ለመመለስ ይህን አደርጋለሁ::'

6"ስለዚህ ለእስራኤል ቤት እንዲህ በል፤ 'ልዑል *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ንስሓ ግቡ! ከጣዖቶቻችሁ ተመለሱ፤ ጸያፍ ተግባራችሁንም ሁሉ ተዉ::"

7" 'ማንኛውም እስራኤላዊ ወይም በእስራኤል የሚኖር ማንኛውም መጻተኛ ራሱን ከእኔ በመለየት ጣዖቶችን በልቡ አኑሮ፣ ክፉቱንም የማሰናከያ ድንጋይ በማድረግ በፊቱ አስቀምጦ ከእኔ ለመጠየቅ ወደ ነቢይ ቢመጣ፣ እኔ ራሴ *እግዚአብሔር* እመልስለታለሁ:: 8ፊቴን በክፉት ወደዚያ ሰው እመልሳለሁ፤ መቀጣጫና መተረቻ አደርገዋለሁ፤

13+10 ኤር4+10፤ 23+13፤50+6፤ ሕዝ7+25፤22+28
13+11 ኢሳ10+11፤ ኢዮ38+23፤ መዝ11+6፤ሕዝ38+22
13+13 ዘፀ9+25፤ ኢሳ10+11፤ ኢዮ 14+19፤38+23፤ ኢሳ30+30፤ ራእ11+19፤16+21
13+14 ኢሳ22+5፤ ኤር6+15፤ሚክ1+6
13+16 ኢሳ57+21፤ ኤር6+14፤ሕዝ7+25
13+17 ቍ2፤ ዘፀ15+20፤ሕዝ4+7፤ 25+2፤28+21፤ ራእ2+20
13+19 ምሳ28+21፤ ኢሳ56+11፤ ኤር44+26፤ ሕዝ20+39፤22+26፤ 36+20፤ 39+7፤ሚክ3+11
13+20 መዝ124+7
13+21 መዝ91+3
13+22 ኢሳ9+15፤ ኤር23+14፤ ሕዝ18+21፤33+14-16
13+23 ነህ6+12፤ መዝ72+14፤ ሕዝ12+24፤ሚክ3+6
14+1 ሕዝ8+1፤ 20+1
14+3 ቍ7፤ ኢሳ1+15፤ሕዝ6+4፤ 7+19፤20+31
14+5 ዘዳ32+15፤ ኤር2+11፤ሕዝ16+45፤ ሆሴ5+7፤ ዘካ11+8
14+6 ነህ1+9፤ ኢሳ2+20፤30+22፤ ኤር3+12፤35+15
14+7 ቍ3፤ ዘፍ 25+22፤ ዘፀ12+48፤20+10፤ ኢሳ8+14፤ ሆሴ4+5፤5+5
14+8 ዘኍ16+38፤ መዝ102+8፤ ኤር42+20፤ ሕዝ5+15፤15+7

[a] 14 ወይም *ከተማው*

ችዋል::

13+10 *ሰላም ሳይኖር፣ 'ሰላም አለ'፤* ቍ16፤ ኤር6+14፤ 8+11 ይመ:: *ኖራ፤* በዕብራይስጥ ይህን ቃል ጠቅሶ የምናገኘው ሕዝቅኤል ብቻ ነው (22+28)፤ ትርጕሙም፣ "የማያጠግብ ነገር" ማለት ነው::

13+11 *ዶፍ ይወርዳል፤* በብሉይ ኪዳን ተደጋግሞ እንደ ተነገረው፣ የእግዚአብሔር ፍርድ ነጐድጓድና ማዕበል እንደ ቀላቀለ ኀይለኛ ዐውሎ ነፋስ ጠራርጎ እንደሚያጠፋ ተገልጾአል (መዝ18+7-15፤ 77+17-18፤ 83+15፤ ኢሳ28+17፤ 30+30፤ ኤር 23+19፤ 30+23 ይመ)::

13+18 *ለእስማታቸው፤* ሴቶቹ የሚያደርጉት ምን እንደ ሆነ በውል ዐይታወቅም፤ ይሁን እንጂ፣ አንድ ዐይነት የአስማት ድርጊት እንደ ሆነ ግልጽ ነው:: ሆኖም ግን፣ መጽሐፍ ቅዱስ የአስማትን ሥራ ይቃወማል::

13+19 *እፍኝ ለማይሞላ ገብስ፤* ለግል ጥቅም ብቻ ሲባል በማንኛውም ሃይማኖታዊ ጕዳይ ውስጥ መሳተፍ የማይገባ መሆኑን መጽሐፍ ቅዱስ በተደጋጋሚ ያወግዛል (ኤር6+13፤ 8+10፤ ሚክ3+5:11፤ ሐሥ8+9-24፤ ቲቶ1+11 ይመ):: አግባብ ስለሆነው ሃይማኖታዊ ተሳትፎን በተመለከተ 2ቆሮ11+7፤ 2ተሰ3+8፤ 1ጢሞ3+3 ይመ:: *በመግደል፤* ሴቶቹ ኢፍትሐዊ ነገሮችን ለመፈጸም፣ ክፉ ኀይላቸውን ተጠቀሙ::

14+1 *ከእስራኤል ሽማግሌዎች፤* "የይሁዳ ሽማግሌዎች" ለሚለው ሐረግ ተለዋጭ ነው (የ8+1 ማብ ይመ)::

14+3 *ጣዖቶቻቸውን፤* የ6+4 ማብ ይመ:: *እንዲጠይቁ፤* ከአንድ ነቢይ ንግር ለማግኘት ሲፈለግ የሚነገር የተለመደ አባባል ነው (2ነገ1+16፤ 3+11፤ 8+8 ይመ)::

14+4 *እኔ እግዚአብሔር ... እመልስለታለሁ፤* ጣዖት ማምለክ የሞት ቅጣትን ያስከትላል (ዘዳ 13+6-18)::

14+6 *ንስሓ ግቡ፤* ከፍርድ ማምለጥ የሚቻል መሆኑን በሌላ ስፍራ የገለጸው ሕዝቅኤል፣ ስለ ንስሓ ካቀረባቸው ሦስት ጥሪዎች ይህ የመጀመሪያው ነው (18+30፤ 33+11 ይመ)::

ከሕዝቤም መካከል አስወግደዋለሁ፤ በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ::

[9]" 'ነቢዩ ትንቢት ይናገር ዘንድ ቢታለል፣ ያንን ነቢይ ያታለልሁ እኔ *እግዚአብሔር* ነኝ፤ ክንዴን በእርሱ ላይ እነሣለሁ፤ ከሕዝቤ ከእስራኤል መካከልም አጠፋዋለሁ:: [10]በደላቸው በራሳቸው ላይ ይሆናል፤ ነቢዩም እርሱን ሊጠይቀው ከመጣው ሰው ጋር እኩል በደለኛ ይሆናል:: [11]ከእንግዲህ የእስራኤል ሕዝብ መንገድ ስቶ ከእኔ አይለይም፤ ተመልሶም በኀጢአቱ ሁሉ ራሱን አያረክስም:: እነርሱ ሕዝቤ ይሆናሉ፤ እኔም ስምላካቸው እሆናለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::"

## የማያመልጡት ፍርድ

[12]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [13]"የሰው ልጅ ሆይ፤ አንድ አገር በእኔ ባለመታመን ቢበድለኝና እኔም እጄን በላዩ ዘርግቼ የምግብ ምንጩን ባደርቅ፣ ራብንም አምጥቼበት ሰውንና እንስሳቱን ብገድል፣ [14]ኖኅ፣ ዳንኤልና[a] ኢዮብ እነዚህ ሦስቱ በዚያ ቢኖሩ እንኳ፣ በጽድቃቸው የሚያድኑት ራሳቸውን ብቻ ነው፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::

[15]"የዱር አራዊትንም በአገሪቱ ላይ ሰድጄ አገሪቱን ሕፃናት አልባ ቢያደርጓትና ከአራዊቱም የተነሣ ምድሪቱ ሰው እስከማያልፍባት ባድማ ብትሆን፣ [16]'እኔ ሕያው *እግዚአብሔርን*' በራሴ እምላለሁ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ እነዚህ ሦስቱ ሰዎች ቢኖሩባት እንኳ፣ ወንዶች ወይም ሴቶች ልጆቻቸውን ማዳን አይችሉም፤ እነርሱ ብቻ ይድናሉ፤ ምድሪቱ ግን ባድማ ትሆናለች::'

[17]"ሰይፍን በአገሪቱ ላይ አምጥቼ፣ 'ሰይፍ በዚህ ምድር ይለፍ' ብል፣ ሰውንና እንስሳን ባጠፋ፣ [18]በሕያውነቴ እምላለሁ ይላል *እግዚአብሔር*፤ እነዚህ ሦስት ሰዎች ቢኖሩባትም እንኳ ራሳቸው ብቻ ይድናሉ እንጂ ወንዶች ወይም ሴቶች ልጆቻቸውን ማዳን አይችሉም::

[19]"ቸነፈርንም በምድሪቱ ላይ ብሰድና ደም በማፍሰስ መዓቴን አውርጄ ሰውንና እንስሳን ባጠፋ፣ [20]በሕያውነቴ በራሴ እምላለሁ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ ኖኅ፣ ዳንኤልና ኢዮብ ቢኖሩባትም እንኳ በጽድቃቸው ራሳቸውን ብቻ ያድናሉ እንጂ ወንዶችን ወይም ሴቶች ልጆቻቸውን አያድኑም::

[21]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ 'ሰውንና እንስሳቱን ለማጥፋት አራቱን አስፈሪ ፍርዶቼን:- ሰይፍን፣ ራብን፣ የዱር አራዊትንና ቸነፈርን በኢየሩሳሌም ላይ በማመጣበት ጊዜ ምንኛ የከፋ ይሆን! [22]ነገር ግን ከዚያ ወጥተው የሚተርፉ ወንዶችና ሴቶች ልጆች አሉ፤ እነርሱም ወደ እናንተ ይመጣሉ፤ እናንተም አካሄዳቸውንና ተግባራቸውን በምታዩበት ጊዜ በኢየሩሳሌም ላይ ስላመጣሁት መከራ፣ ስላደረስሁባትም አስከፊ ነገር ሁሉ ትጽናናላችሁ:: [23]አካሄዳቸውንና ተግባራቸውን በምታዩበት ጊዜ፣ ትጽናናላችሁ፤ አንዳች ነገር በከንቱ እንዳላደረግሁ ትረዳላችሁና፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::' "

## የማይረባው የወይን ግንድ

**15** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ የወይን ግንድ በዱር ካሉት ዛፎች ሁሉ ቅርንጫፍ የሚሻለው በምንድን ነው? [3]የሚጠቅም ነገር ለመሥራት ከግንዱ አንዳች ተወስዶ ያውቃልን? ዕቃ የሚንጠለጠልበትስ ኵላብ ከእርሱ ይበጃልን? [4]እንዲነድ እሳት ላይ ከተጣለ በኋላ፣ እሳቱ ጫፍና ጫፉን አቃጥሎ፣ መኻሉን ከለበለበው፣ ለአንዳች ነገር ይጠቅማልን? [5]እንግዲህ ደኅና ሆኖ ሳለ ለምንም ነገር ካልጠቀመ፣ እሳት ካቃጠለውና ከለበለበው በኋላ የቱን ያህል የሚረባ ይሆን!

[6]"ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ከዱር ዛፎች መካከል የወይን ግንድ እንዲነድ ለእሳት አሳልፌ እንደ ሰጠሁ፣ እንዲሁ የኢየሩሳሌምን ነዋሪዎች አሳልፌ እሰጣለሁ:: [7]ፊቴን በከፋት ወደ እነርሱ

[a]14 ወይም *ዳኔል፤* የዕብራይስጡን ቃል አጻጻፍ ስንመለከት ነቢዩ ዳንኤልን ሳይሆን ሌላን ሰው የሚያመለክት ነው፤ እንዲሁም ቍ 20

14+9 1ነገ22+23፤ 2ዜና18+22፤ ኢሳ63+17፤ኤር4+10፤ 14+15፤ዘካ13+3
14+11 ኢሳ51+16፤ ሕዝ11+19-20፤ 37+23፤48+11
14+13 ዘሌ26+26፤ ምሳ13+21፤ ሕዝ5+16፤6+14፤15+8
14+14 ቍ 20፤ ዘፍ6+8:9፤ኢዮ1+1፤ 42+9፤ኤር15+1፤ ሕዝ3+19፤18+20፤ 28+3፤ዳን1+6፤6+13
14+15 ዘሌ26+22፤ ሕዝ5+17
14+16 ዘፍ19+29፤ ሕዝ 18+20
14+17 ዘሌ26+25፤ ኤር25+27፤42+16፤ ሕዝ25+13፤ሶፎ1+3
14+19 ኢሳ34+3፤ ኤር14+12፤ሕዝ7+8፤ 38+22
14+20 ቍ 14
14+21 ዘኍ33+4፤ 2ሳሙ24+13፤ኢሳ 31+8፤34+6፤66+16፤ ኤር14+12፤15+3፤ 27+8፤ሕዝ5+17፤ 21+13፤19፤33+27፤ አሞ4+6-10፤ራእ6+8
14+22ኤር41+16፤ ሕዝ12+16፤20+43፤ 31+16፤32+31
14+23ኤር22+8-9፤ ሕዝ8+6-18፤9+9
15+2 መዝ80+8-16፤ ኢሳ5+1-7፤27+2-6፤ ኤር2+21፤ሆሴ10+1፤ ዮሐ15+2
15+3 ኢሳ22+23፤ ኤር13+10
15+4 ሕዝ17+3-10፤ 19+14፤ዮሐ15+6
15+7 ዘሌ26+17፤ መዝ34+16፤ ኢሳ24+18፤ ሕዝ5+2:4፤14+8፤ አሞ9+1-4

14+9 *ቢታለል፤* ከመለኮታዊ ኀይል የመጣ ማለት ነው (3+20፤ ከ1ነገ22+19-23 ጋር ያነጻጽሩ)::

14+14:20 *ኖኅ፣ ዳንኤልና ኢዮብ፤* የታወቁ የጥንት ዘመን ሰዎች ናቸው፤ የተመረጡትም በጽድቃቸው ነው:: አማራጭ ትርጕሙ እንደሚያመለክተው ይኸኛው ዳንኤል በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሚገኘው ነቢዩ ዳንኤል ሳይሆን፣ "የተከበረ ዳንኤል" ተብሎ የሚታወቅ ሌላ ሰው ነው፣ ከዚህ የተነሣም አንዳንድ ሰዎች፣ ሕዝቅኤልና ነቢዩ ዳንኤል በአንድ ወቅት አብረው የኖሩ ስለ ሆነ ሕዝቅኤል በዘመኑ ስለነበረው ዳንኤል የሚጽፍበት ምክንያት የለም ይላሉ (ዳን1+1 ይመ)፤ ይህ ስሙ በመጽሐፍ ቅዱስ የተጠቀሰው ዳንኤል ከሆነም፣ ከኖኅና ከኢዮብ ጋር ስሙ አብሮ መጠራቱ ጽድቅን በተመለከተ ብቻ ሳይሆን በትድግናም ከእነርሱ ጋር ተመሳሳይ ነው:: ይህ ደግሞ ነቢዩ ሕዝ ቅኤል በአጽንዖት ከሚገልጸው ሐሳብ አንዱ ክፍል ነው::

14+20 *ወንዶችን ወይም ሴቶች ልጆችን፤* እግዚአብሔር ወደ አንድ ሕዝብ ወይም ወደ አንድ መንግሥት በፍርድ በሚመጣበት ጊዜ፣ አንዱ በሌላው ጽድቅ መዳን አይችልም፤ ስለዚህም የወላጆች ጽድቅ ለልጅ አይተርፍም::

14+21 *አራቱን አስፈሪ ፍርዶቼን፤* የ1+5 ማብ ይመ:: *ሰይፍን፣ ራብን፣ የዱር አራዊትንና ቸነፈርን፤* ይህን በዮሐንስ ራእይ ከተጠቀሱት ፈረሰኞች ጋር ያነጻጽሩ (ራእ6+1-8 ይመ፤ በተለይም ራእ6+8 ይመ)::

14+23 *ትጽናናላችሁ፤* ባቢሎን ያሉትን ምርኮኞች የሚመለከት ነው:: በምርኮ የሄዱት፣ ከኢየሩሳሌም ወደ ባቢሎን የመጡትን ሰዎች ክፋት ሲመለከቱ፣ እግዚአብሔር በከተማዪቱ ላይ ያወረደው ፍርድ ተገቢ መሆኑን ይገነዘባሉ::

15+2 *የወይን ግንድ፤* እስራኤል የወይን ተክል ተብላ ተጠርታለች በመዝ80+8-13 ላይ ይመ፤ ከሉቃ20+9-19፤ ዮሐ 15+1-17 ጋር ያነጻጽሩ::

15+3 *ዕቃ የሚንጠለጠልበትስ ኵላብ ከእርሱ ይበጃልን?* ኢሳ22+23-25 ይመ::

15+4 *ለአንዳች ነገር ይጠቅማልን?* ኢሳይያስና (5+1-7) ኤርምያስ (2+21) እስራኤል መልካም ፍሬ ማፍራት ስላልቻለች፣ አምላክ ክፉኛ ያዘነባት መሆኑን ሲገልጹ፣ ሕዝቅኤል

እመልሳለሁ፤ ከእሳት ቢያመልጡም፣ ገና እሳት ይበላቸዋል። ፊቴን በክፋት ወደ እነርሱ በመለስሁ ጊዜ፣ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ። [8]ታማኝ ካለመሆናችሁ የተነሣ ምድሪቱን ባድማ አደርጋታለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።"

## ኢየሩሳሌም ታማኝ ስላለመሆኗ የተሰጠ ተራዛሚ ተለዋጭ ዘይቤ

**16** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ለኢየሩሳሌም አስጸያፊ ተግባሯን ፊት ለፊት ንገራት፤ [3]እንዲህም በል፤ 'ልዑል እግዚአብሔር ኢየሩሳሌምን እንዲህ ይላታል፤ "ዘርሽና ትውልድሽ ከከነዓን ምድር ነው፤ አባትሽ አሞራዊ፣ እናትሽም ኬጢያዊት ነበሩ። [4]በተወለድሽበት ቀን እትብትሽ አልተቈረጠም፤ ንጹሕ እንድትሆኚ በውሃ አልታጠብሽም፤ በጨው አልታሸሽም፤ በጨርቅም አልተጠቀለልሽም። [5]በርኅራኄ ዐይን ተመልክቶሽ ወይም አዝኖልሽ ከእነዚህ አንዱን እንኳ ያደረገልሽ ሰው አልነበረም፤ ይልቁንም በተወለድሽበት ቀን ተንቀሽ ስለ ነበር ሜዳ ላይ ተጣልሽ።

[6]" 'እኔም በዚያ ሳልፍ፣ በደምሽ ውስጥ ወዲያ ወዲህ ስትንፈራገጪ አየሁሽ፤ በደምሽም ውስጥ ተኝተሽ ሳለሽ፣ "በሕይወት ኑሪ!"[ж] አልሁሽ። [7]ሜዳ ላይ እንዳለ ቡቃያ አሳደግሁሽ፤ አንቺም አደግሽ፤ ብርቅ ዕንቍ ሆንሽ[ፐ]። ጡቶችሽ አጐጠጐጡ፤ ጠጕርሽም አደገ፤ ነገር ግን ከእናትሽ ማሕፀን እንደ ወጣሽ ዕርቃንሽን ነበርሽ።

[8]"ዳግመኛም በአጠገብሽ በማልፍበት ጊዜ ወደ አንቺ ተመለከትሁ፤ ለመፈቀርም እንደ ደረስሽ ባየሁ ጊዜ፣ የመጐናጸፊያዬን ዘርፍ በላይሽ ዘርግቼ ዕርቃንሽን ሸፈንሁ። ማልሁልሽ፤ ከአንቺም ጋር ቃል ኪዳን ተጋባሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ አንቺም የእኔ ሆንሽ።

[9]"በውሃ አጠብሁ[ሠ] ከደም አጠራሁሽ፤ ዘይትም ቀባሁሽ። [10]ወርቀ ዘቦ አለበስሁሽ፤ ምርጥ ቈዳ ጫማም አደረግሁልሽ፤ ያማረ በፍታ አለበስሁሽ ውድ መደረቢያም አጐናጸፍሁሽ። [11]በጌጣጌጥ አንቈጠቈጥሁሽ፤ በእጅሽ አንባር፣ በዐንገትሽም ድሪ አጠለቅሁልሽ፤ [12]በአፍንጫሽ ቀለበት፣ በጆሮሽ ጕትቻ፣ በራስሽም ላይ ውብ አክሊል አደረግሁልሽ፤ [13]በወርቅና በብር አጌጥሽ፤ ልብስሽም ያማረ በፍታ፣ ሐርና ወርቀ ዘቦ ነበር፤ ምግብሽም የላመ ዱቄት፣ ማርና የወይራ ዘይት ነበር። እጅግ ውብ ሆንሽ፤ ንግሥት ለመሆንም በቃሽ። [14]እኔ ከሰጠሁሽ ሞገስ የተነሣ ውበትሽ ፍጹም በመሆኑ ዝናሽ በአሕዛብ መካከል ገነነ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።

[15]" 'ነገር ግን በውበትሽ ተመካሽ፤ ዝናሽንም ለአመንዝራነት ተጠቀምሽበት፤ ከዐላፊ አግዳሚው ጋር ያለገደብ አመነዘርሽ ውበትሽም

15፥8 ሕዝ14፥13፤ 17፥20፤18፥24
16፥2 ኢሳ57፥12፤ ሕዝ8፥17፤20፥4፤ 22፥2፤23፥36
16፥3 ቍ45፤ ዘፍ10፥15፤ 11፥25-29፤12፥18፤ 15፥16፤ዘዳ7፥1፤ ኢሱ24፥14-15፤ ሕዝ21፥30
16፥4 ሆሴ2፥3
16፥6 ቍ22፤ ዘፀ19፥4፤ ሕዝ18፥23፡32
16፥7 ዘፀ1፥7፤ ዘፀ1፥10
16፥8 ቍ59፤ ሩት3፥9፤ኤር2፥2፤ 11፥10፤ሆሴ2፥7፡ 19-20፤ሚል2፥14
16፥9 ሩት3፥3
16፥10 ቍ18፤ ዘፀ26፥36፤ኢሳ3፥23፤ 19፥9፤ሕዝ27፥16
16፥11 ዘፍ41፥42፤ መዝ73፥6፤ኢሳ3፥19፤ ኤር4፥30፤ ሕዝ23፥40፡42
16፥12 ዘፍ35፥4፤ ምሳ1፥9፤ኢሳ3፥19፡ 21፤28፥5፤ ኤር13፥18
16፥13 ዘዳ32፥13 -14፤1ሳሙ10፥1፤ 1ነገ4፥21፤አስ2፥9፡ 17፤5፥1
16፥14 1ነገ10፥24፤ አስ1፥11፤መዝ48፥2፤ ሰቆ2፥15፤ሕዝ5፥5
16፥15 ቍ25፤ ኢሳ57፥8፤ኤር2፥20፤

ж6 ጥቂት የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ሰብዓ ሊቃናትና ሱርስቱ እንዲሁ ሲሆኑ አብዛኞቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ግን "በሕይወት ኑሪ" በደምሽ ውስጥ ተኝተሽ ሳለሽ "በሕይወት ኑሪ" አልሁሽ ይላሉ
ፐ7 ወይም የበሰልሽ ሆንሽ
ሠ9 ወይም በውሃ አጠብሁሽ

ደግሞ ኢየሩሳሌም ፈጽሞ የማትጠቅም በመሆንዋ ያለቅሳል።

15፥7 *ከእሳት ቢያመልጡም፤* በ 597 ዓ.ቅ.ክ. ኢየሩሳሌም መያዟን ሲያመለክት፣ ራሱ ሕዝቅኤልም ከሕዝቡ ጋር አብሮ መማረኩን ያሳያል (1፥2፤ 2ነገ24፥10-16 ይመ)። *ገና እሳት ይበላቸዋል፤* ከዚህ የሚበልጥ ሌላ መከራ የሚመጣባቸው መሆኑን የሚያስገነዝብ አስፈሪ ትንቢት ነው፤ ይህም ከ586 ዓ.ቅ.ክ. በፊት የነበረ ዋናው የሕዝቅኤል መልእክት ነው (5፥2፡4፤ 10፥2፡7 ይመ)።

*16፥3፤* ከዘዳ26፥5 ጋር ያነጻጽሩ። *ዘርሽና ትውልድሽ፤* እስራኤላውያን ኢየሩሳሌምን ከመያዛቸው በፊት፣ ኢየሩሳሌም የቆየ የብዙ ምእተ ዓመት ያላት ከተማ ነች (ዘፍ14፥8)፤ የእስራኤላውያንን ወረራ ብዙ ጊዜ ተቋቁማ ነበር (ኢሱ15፥63)፤ ሆኖም ንጉሥ ዳዊት ከያዛት በኋላ ሙሉ በሙሉ የእስራኤላውያን መዲና ለመሆን በቅታለች (2ሳሙ5፥6-9)። *አባትሽ ... እናትሽም፤* ኢየሩሳሌም ቀድሞውም የእስራኤል አለመሆን ለመግለጽ እንጂ፣ አንዱን ግለሰብ በተለይ ለማመልከት የገባ አይደለም። *አሞራዊ፤* ከቍ45 ጋር ያነጻጽሩ። እንደ ከነዓናውያን፣ አሞራውያንም ከቅድመ እስራኤላውያን በፊት በፓሌስቲና ምድር የነበሩ ሴማውያን ናቸው (ዘፍ48፥22፤ ኢሱ5፥1፤ 10፥5፤ መሳ1፥34-36 ይመ)። *ኬጢያዊ፤* በሁለት ሺህ ዓ.ቅ.ክ. ገደማ ከትንሹ እስያ ፈልሰው፣ በከነዓን የሰፈሩና ከሴም ነገድ ያልሆኑ ሕዝቦች ናቸው (ዘፍ23፥10-20፤ 26፥34፤ 1ሳሙ26፥6፤ 2ሳሙ11፥2-27፤ 1ነገ11፥1 ይመ)።

16፥4 *በጨው አልታሸሽም፤* ይህ ልማድ በፍልስጥኤም ምድር በሚኖሩ የዐረብ ገበሬዎች ዘንድ እስከ 1918 ዓ.ም. ድረስ ቈይቶ እንደ ነበር አንዳንድ ጸሓፊዎች ይመሰክራሉ፤ ይህም ልማድ ተመሳሳይ ባሕል ባላቸው በሌሎችም አገሮች እስከ ዛሬ ድረስ ይጠበቃል። በአገራችንም ቍስልንና ዕብጠትን በጨው አጥቦ ማሰር የተለመደ ባሕላዊ ሕክምና ነው። *በጨርቅም አልተጠቀለልሽም፤* ከሉቃ2፥7 ጋር ያነጻጽሩ።

16፥5 *በሜዳ ላይ ተጣልሽ፤* እንድትሞት ተጥላለች ማለት ነው፤ በቀድሞ ጊዜ በአረማውያን ዘንድ የተለመደው ሕፃናትን አውጥቶ የመጣል ልማድ በእስራኤላውያን ዘንድ እጅግ የተጠላ ነበር።

16፥6 *በደምሽ፤* ልጅ ሲወለድ የሚፈሰውን ደም ያመለክታል። *በሕይወት ኑሪ፤* እግዚአብሔር ለሰው ሁሉ ያለው ዐላማ በዚህ ሐረግ ተገልጾአል (18፥23፡32፤1ጢሞ2፥4፤2ጴጥ3፥9 ይመ)።

16፥7 *ጠጕርሽም፤* ወንድ ልጅ ለዐቅመ አዳምና ሴት ልጅም ለዐቅመ ሔዋን በደረሱ ጊዜ የሚበቅለውን ጠጕር ነው።

16፥8 *የመጐናጸፊያዬን ዘርፍ በላይሽ ዘርግቼ፤* የጋብቻን ሁኔታ የሚያመለክት ትእምርታዊ አባባል ነው (የዘዳ 22፥30፤ ሩት3፥9 ማብ ይመ)። *ቃል ኪዳን፤* ሴቲቱ የምታመለክተው ኢየሩሳሌምን ስለ ሆነ፣ ይህ ኪዳን የጋብቻ እንጂ የሲና ኪዳን አይደለም (ሚል2፥14 ይመ)።

16፥9 *ከደም፤* የወር አበባን የሚያመለክት ነው፤ ይህም ለዐቅመ ሔዋን መድረሷን ያረጋግጣል (የቍ7 አማራጭ ትርጕሙን ይመ)።

16፥10 *ወርቀ ዘቦ ... ቈዳ ጫማ ... ያማረ በፍታ፤* ምርጥ የሆኑ አልባሳትን የሚያመለክቱ ናቸው። *ወርቀ ዘቦ፤* 27፥16፡24 ይመ። በኅብረ ቀለም ያሸበረቀ ለአንዲት ንግሥት የሚሆን ልብስ ነው (መዝ45፥14 ይመ)። *ቈዳ ጫማ፤* ተመሳሳይ ከሆነ ቈዳ የማደሪያው ድንኳን መሸፈኛ ይሠራል ("የአቆስጣ ቈዳ" ዘፀ25፥5፤ 26፥14)።

16፥11 *በእጆችሽ አንባር፤* ዘፍ24፥22 ይመ።

16፥12 *ቀለበት፤* አፍንጫን የሚጐዳ ሳይሆን፣ በአፍንጫ ላይ የሚጣበቅ ወይም የሚንጠለጠል ጌጥ ነው (ዘፍ24፥47 ይመ)። *ጕትቻ፤* ዘኍ31፥50 ይመ፤ ከዘፍ35፥4፤ ዘፀ32፥2-3 ጋር ያነጻጽሩ። *አክሊል፤* ሙሽራ በሰርጉ ጊዜ በራሱ ላይ የሚደፋው አክሊል ነው (ወንድ ሙሽራ ስለሚደፋው አክሊል ማሕ3፥11 ይመ)።

16፥13 *በወርቅና በብር፤* ከሆሴ2፥8 ጋር ያነጻጽሩ። *የላመ ዱቄት፤* ለመሥዋዕት የሚያገለግል ሲሆን፣ በዐይነቱ ምርጥ ዱቄት ማለት ነው (ቍ19፤ 46፥14 ይመ)። *የወይራ ዘይት፤* ከሆሴ2፥8 ጋር ያነጻጽሩ፤ ስለ ማርና ስለ ዘይት መቀላቀል ዘዳ32፥13 ይመ። *እጅግ ውብ ሆንሽ፤* ከኤፌ5፥27 ጋር ያነጻጽሩ።

16፥14 *ዝናሽ ... ገነነ፤* ይህ የሆነው፣ በተለይ በንጉሥ ዳዊትና በንጉሥ ሰሎሞን ዘመነ መንግሥት ነበር።

16፥15 *ለአመንዝራነት፤* በመንፈሳዊ ሕይወት ከእግዚ

ለማንም ሆነ::[ሙ] [16]ከልብስሽ አንዳንዱን ወስደሽ የምታመነዝሪበትን መስገጃ ስፍራ አስጌጥ ሽበት፤ እንዲህ ዐይነት ነገር ከዚህ ቀደም አልታየም፤ ወደፊትም አይኖርም:: [17]ከሰጠሁሽ ወርቄና ብሬ የተሠራውን ምርጥ ጌጣጌጥ ወስደሽ የወንድ ምስሎች ለራስሽ አበጀሽ፤ ከእነርሱም ጋር ዝሙት ፈጸምሽ:: [18]ወርቀዘቦ ልብስሽን ወስደሽ ደረብሽላቸው፤ ዘይቴንና ዕጣኔንም በፊታቸው አቀረብሽ:: [19]እንድትበዪ የሰጠሁሽን ምግብ ይኸውም ምርጡን ዱቄት፣ ማሩንና የወይራ ዘይቱን መልካም መዐዛ ያለው ዕጣን አድርገሽ አቀረብሽላቸው፤ እንዲህ ያለ ነገር ተፈጽሞአል፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::

[20]" 'ለእኔ የወለድሻቸውን ወንዶችና ሴቶች ልጆችሽን እንዲበሏቸው ለምስሎቹ ሠዋሽላቸው፤ አመንዝራነትሽ አንሶ ነውን? [21]ልጆቼን ዐርደሽ ለጣዖት መሥዋዕት አድርገሽ አቀረብሻቸው::[ሠ] [22]በእነዚህ አስጸያፊ ተግባሮችሽና አመንዝራነትሽ ሁሉ፣ ከእናትሽ ማሕፀን እንደ ወጣሽ ዕርቃንሽን ሆነሽ በደምሽ ውስጥ ስትንፈራገጪ የነበርሽበት የሕፃንነትሽ ወራት ትዝም አላለሽ!::

[23]" 'ወዮ! ወዮልሽ! ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ ከሌላው ክፋትሽ ሁሉ በተጨማሪ፣ [24]ለራስሽ ጉብታን አበጀሽ፤ በየአደባባዩም የማምለኪያ ኰረብታ ሠራሽ:: [25]በየመንገዱ መጠምዘዣ ላይም የመስገጃ ኰረብታ አበጀሽ፤ ገላሽን ለዐላፊ አግዳሚው በማቅረብና አመንዝራነትሽን በማብራከት ውበትሽንም አረከስሽ:: [26]ዘማውያን ከሆኑ ግብፃውያን ጎረቤቶችሽ ጋር አመነዘርሽ፤ ገደብ በሌለው የዝሙት ተግባርሽም ለቍጣ አነሣሣሽኝ:: [27]ስለዚህ ክንዴን በአንቺ ላይ አንሥቼ ድርሻሽን ቀነስሁ፤ ከክፉ መንገድሽም የተነሣ በብልግናሽ ለሚያፍሩ ጠላቶችሽ ለፍልስጥኤማውያን ሴቶች ልጆች አሳልፌ ሰጠሁሽ:: [28]ገና ስላልረካሽም ከአሦራውያን ጋር ደግሞ አመነዘርሽ፤ ከዚያም በኋላ እንኳ አልረካሽም:: [29]ርኩሰትሽንም እስከ ነጋዴዎች ምድር እስከ ባቢሎን[ረ] ድረስ አበዛሽ፤ ያም ሆኖ አልረካሽም::

[30]" 'እንደ ዐይን አውጣ አመንዝራ ይህን ሁሉ መፈጸምሽ ምን ዐይነት ደካማ ልብ ቢኖርሽ ነው! ይላል ጌታ እግዚአብሔር:: [31]በየመንገዱ መጠምዘዣ ላይ ጉብታሽን ባበጀሽና በየአደባባዩም መስገጃ ኰረብታ በሠራሽ ጊዜ እንደማንኛውም ዝሙት አዳሪ አልነበርሽም፤ ምክንያቱም ዋጋ አላስከፈልሽም::

[32]" 'አንቺ ከገዛ ባሏ ይልቅ ሌሎችን የምታስተናግድ አመንዝራ ነሽ! [33]ማንኛዋም አመንዝራ ሴት ዋጋ ይከፈላታል፤ አንቺ ግን ለወዳጆችሽ ሁሉ ስጦታ ታበረክቻለሽ፤ ከየአቅጣጫው መጥተው ከአንቺ ጋር ያመነዝሩ ዘንድ እጅ መንሻ ታቀርቢላቸዋለሽ:: [34]ስለዚህ ያንቺ ግልሙትና ከሌሎቹ የተለየ ነው፤ ማመንዘር የሚሻ ማንም ሰው፣ አንቺን አሳዶ ማግባባት አያስፈልገውም:: ዋጋ ትከፍ ያለሽ እንጂ አይከፈልሽም፤ አንቺ የሌሎች ፍጹም ተቃራኒ ነሽ::

[35]" 'አንቺ አመንዝራ ሆይ፤ እንግዲህ *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሚ! [36]ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ሀብትሽን[ሰ] ስላፈሰስሽ፣ ከወዳጆችሽ ጋር ያለ ገደብ ስላመነዘርሽና ዕርቃንሽን ስለ ገለጥሽ፣ ስለ አስጸያፊ ጣዖቶችሽ ሁሉና ለእነርሱም የልጆችሽን ደም ስላቀረብሽ፣ [37]በዚህ ምክንያት ደስ የተሰኘሽባቸውን ወዳጆችሽን፣ የወደድሻቸውንና የጠላሻቸውን ሁሉ እሰበስባለሁ፤ ከየአቅጣጫው ሁሉ በዙሪያሽ እሰበስባቸዋለሁ፤ በፊታቸው ዕርቃንሽን እገልጣለሁ፤ እነርሱም ኀፍረተ ሥጋሽን ሁሉ ያያሉ:: [38]ለአመንዝራና ለነፍስ ገዳይ ሴቶች የሚገባውን ፍርድ እፈርድብሻለሁ፤ በመዓቴና በቅናቴ እስከ ደም እበቀልሻለሁ:: [39]ለወዳጆችሽ አሳልፌ እሰጥሻለሁ፤ እነርሱም ጉብታሽንና የማምለኪያ ኰረብታሽን ያፈርሳሉ፤ ልብስሽን ይገፉሻል፤ ምርጥ ጌጣጌጥሽን ይቀሙሻል፤

ሕዝ 23+3፤27+3
16+16 2ነገ23+7፤ ኢሳ57+7
16+17 ሕዝ7+20፤ ሆሴ2+13
16+18 ኤር44+5
16+19 ሆሴ2+8
16+20 ዘፀ13+2፤ መዝ106+37-38፤ ኢሳ57+5፤ኤር7+31፤ ሕዝ23+37
16+21 2ነገ17+17፤ ኤር19+5፤
16+22 ቍ6፤ መዝ25+7፤88+15፤ ኤር2+2፤ሆሴ2+3፡15፤ 11+1
16+23 ሕዝ24+6
16+24 ቍ31፤ መዝ78+58፤ ኢሳ57+7፤ኤር2+20፤ 3+2፤44+21፤ ሕዝ20+28
16+25 ቍ15፤ ምሳ9+14፤ኤር3+2
16+26 1ነገ14+9፤ ኢሳ23+17፤57+8፤ ኤር3+1፤11+15፤ ሕዝ8+17፤20+8፤ 23+19-21
16+27 2ዜና28+18፤ ኤር34+20፤ ሕዝ20+33፤25+13
16+28 2ነገ16+7፤ ኢሳ57+8
16+29 ኤር3+1፤ ሕዝ23+14-17፤ ናሆ3+4
16+30 ኤር3+3
16+31 ቍ24
16+33 ዘፍ30+15፤ ኢሳ30+6፤57+9፤ ሆሴ8+9-10
16+36 ኤር19+5፤ ሕዝ23+10
16+37 ኢሳ47+3፤ ኤር13+22፤ ሕዝ23+22፤ሆሴ2+3፡ 10፤8+10፤ራእ17+16
16+38 ዘፍ38+24፤ ዘሌ20+10
16+39 2ነገ18+11፤ ሕዝ21+31፤ሆሴ2+3

[ሙ]15 ከአብዛኞዎቹ የጥንት የዕብራይስጥ ቅጆች ጋር ተመሳሳይ ሲሆን አንድ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጅ ግን (አንዳንድ የሰብዓ ሊቃናት የጥንት ቅጆችን ይመ) *ከዐላፊ አግዳሚ ...አመንዝርሽ፤ እንዲህ ያለው ነገር መሆን የለበትም* ይላል

[ሠ]21 ወይም *በእሳት ውስጥ አሳለፋችኋቸው*

[ረ]29 ወይም *ካላዲያ*

[ሰ]36 ወይም *ምኞትሽን*

አብሔር ዘወር ማለትንና አረማውያን የሆኑት ከከነዓናውያን ልጅ ለመውለድ ሲፈልጉ በቤተ ጣዖት የሚፈጽሙትን አስነዋሪ ተግባር የሚያመለክት ነው (ከኤር3+1-5፤ ሆሴ4+13-14፤ 9+1 ጋር ያነጻ ጽሩ):: *ከዐላፊ አግዳሚ ጋር፤* ከዘፍ38+14-16 ጋር ያነጻጽሩ::

16+16 *ከልብስሽ፤* እግዚአብሔር አስቀድሞ ለኢየሩሳሌም የሰጣትን ስጦታ ሁሉ፣ ለምንዝርና ተጠቀመችበት:: አንዳንዶቹ የልብስ ዐይነቶች ለአሼራ ጣዖት ሥርዐተ አምልኮ ይውሉ ነበር (2ነገ23+7 ይመ)፤ *መጋረጃ* ወይም የዐልጋ ምንጣፍ ሆነው አገልግለው ሊሆን ይችላል (አሞ2+7-8)::

16+17 *የወንድ ምስሎች፤* የወንድን ኀፍረተ ሥጋ የሚያሳዩ ምስሎች ወይም ሥዕሎች ለማለት ነው (23+14 ይመ)::

16+20 *ወንዶችና ሴቶች ልጆችሽን ... ሠዋሽላቸው፤* 20+26፡31፤ 23+37፤ 2ነገ21+6፤ 23+10፤ ኤር7+31፤ 19+5፤ 32+35 ይመ:: ሕፃናትን መሥዋዕት አድርጐ ማቅረብ የተከለከለ መሆኑ በዘሌ18+21፤ 20+2፤ ዘዳ12+31፤18+10 ላይ ተደንግጓል::

16+24 *ጉብታ ... የማምለኪያ ኰረብታ፤* ከከተማ ውጪ በነበሩት ከፍታ ቦታዎች ላይ ሲደረግ የነበረው አምልኮተ ጣዖት (ቍ15)፣ ኢየሩሳሌም ከተማ ውስጥ መደረግ ተጀመረ::

16+26 *ዘማውያን፤* በዕብራይስጡ ሥዕላዊ በሆነ መንገድ ሲገለጽ፣ "ከሚገባ በላይ ትልቅ ብልት ካላቸው ጋር" የሚል ትርጉም አለው፤ የአገላለጹ ከባድነት የሚያመለክተው፣ እግዚአብሔርና ሕዝቅኤል በኢየሩሳሌም አስነዋሪ ድርጊት እጅግ ማዘናቸውን ነው::

16+33 *ለወዳጆች ሁሉ ስጦታ ታበረክቻለሽ፤* የኢየሩሳሌም ጠማማነት ከምንዝርናና ከተራ ግልሙትና የከፋ ለመሆኑ፣ በዚህ ስፍራ ተገልጾአል (ቍ34 ይመ)::

16+37 *ዕርቃንሽን እገልጣለሁ፤* በቍ8 ላይ ተገልጾ ለነበረው የጋብቻ ሁኔታና ጥሎሽ በተቃርኖ የተገለጸ ሲሆን፣ በቍ7 ላይ ለተገለጸውም አቀባበል ምላሽ ነው::

16+38 *እፈርድብሻለሁ፤* ቅጣቱ ሞት ነው (ዘሌ20+10፤ ዘዳ22+22 ይመ)፤ ይህም በድንጋይ በመውገር (ቍ40፤ ዘዳ 22+21-24፤ ዮሐ8+5-7 ይመ) ወይም በእሳት በማቃጠል (ዘፍ 38+24) የሚፈጸም ነው::

16+39 *ጉብታሽንና የማምለኪያ ኰረብታሽን፤* በከተማ ውስጥ ያሉትን የጣዖት ማምለኪያ ስፍራዎችን የሚያመለክት ነው (ቍ24 ይመ)::

ዕርቃንሽንና ባዶ እጅሽን ያስቀሩሻል:: [40]ሕዝብ ያነሣሡብሻል፤ በድንጋይ ይወግሩሻል፤ በሰይፍ ይቈራርጡሻል፤ [41]ቤቶችሽን ያቃጥላሉ፤ በብዙ ሴቶችም ፊት ቅጣት ያመጡብሻል:: ግልሙትናሽን አስተውሻለሁ፤ ከእንግዲህም ለወዳጆችሽ ዋጋ አትከፍዪም:: [42]በዚህም በአንቺ ላይ የነበረው ቍጣዬ ይበርዳል፤ የቅናቴ ቍጣም ከአንቺ ይርቃል:: እኔም ዝም እላለሁ፤ ከእንግዲህም አልቈጣም::

[43]“ ‘በእነዚህ ነገሮች አስቈጣሽኝ እንጂ የልጅነትሽን ወራት አላሰብሽም፤ ስለዚህ የሥራሽን እከፍልሻለሁ፤ ይላል ልዑል *እግዚአብሔር*:: በሌላው አስጸያፊ ተግባርሽ ሁሉ ላይ ዘማዊነትን አልጨመርሽምን?

[44]“ ‘በምሳሌ የሚናገር ሁሉ፣ “ሴት ልጅ በእናቷ ትወጣለች” እያለ ይመስልብሻል:: [45]አንቺ ባሏንና ልጆቿን የምትጸየፍ የእናትሽ ልጅ ነሽ፤ ባሎቻቸውንና ልጆቻቸውን የሚጸየፉ የእኅቶችሽ እኅት ነሽ:: እናታችሁ ኬጢያዊት፣ አባታችሁም አሞራዊ ነበሩ:: [46]ታላቂቱ እኅትሽ ከአንቺ በስተ ሰሜን ከሴት ልጆቿ ጋር የምትኖረው ሰማርያ ናት፤ ታናሺቱ እኅትሽም ከአንቺ በስተ ደቡብ ከሴት ልጆችዋ ጋር የምትኖረው ሰዶም ናት:: [47]አንቺም በእነርሱ መንገድ መሄድና አስጸያፊ ተግባራቸውን መከተል ብቻ ሳይሆን፣ ከእነርሱ ይልቅ ፈጥነሽ ምግባረ ብልሹ ሆንሽ:: [48]እኔ ሕያው እግዚአብሔርን! በራሴ እምላለሁ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ አንቺና ሴት ልጆችሽ ያደረጋችሁትን እኅትሽ ሰዶምና ልጆቿ እንኳ አላደረጉትም::

[49]“ ‘እነሆ የእኅትሽ የሰዶም ኀጢአት ይህ ነበር፤ እርሷና ሴት ልጆቿ እብሪተኞች፣ ጥጋበኞችና ደንታ ቢሶች ነበሩ፤ ድኾችንና ችግረኞችንም አይረዱም ነበር:: [50]ኵራተኞች ነበሩ፤ በፊቴ አስጸያፊ ተግባር መፈጸማቸውን ባየሁ ጊዜም አስወገድኋቸው:: [51]ሰማርያ አንቺ ያደረግሽውን ኀጢአት ግማሹን እንኳ አልሠራችም:: አንቺ ግን ከእነርሱ የባሰ አስጸያፊ ተግባር በመፈጸምሽ፣ በዚህ ሁሉ እኅቶችሽን ጻድቃን አስመሰልሻቸው:: [52]እኅቶችሽን እንደ ጻድቃን በማስቈጠርሽ፣ ዕፍረትሽን ተከናነቢ፤ ኀጢአትሽ ከኀጢአታቸው የከፋ ስለ ሆነ፣ እነርሱ ከአንቺ ይልቅ ጻድቃን ሆኑ:: እንግዲህ እኅቶችሽን ጻድቃን ስላስመሰልሻቸው፣ አንቺ ተዋረጂ፤ ዕፍረትሽንም ተከናነቢ::

[53]“ ‘ነገር ግን የሰዶምንና የሴት ልጆቿን፣ እንዲሁም የሰማርያንና የሴት ልጆቿን ምርኮ እመልሳለሁ፤ የአንቺንም ምርኮ የእነርሱን በምመልስበት ጊዜ እመልሳለሁ:: [54]ይህም የሚሆነው ለእነርሱ መጽናኛ በመሆንሽ እንድትዋረጂና ባደረግሽው ሁሉ እንድታፍሪ ነው:: [55]እኅቶችሽ ሰዶምና ሴት ልጆቿ እንዲሁም ሰማርያና ሴት ልጆቿ ቀድሞ ወደ ነበሩበት ሁኔታ ይመለሳሉ፤ አንቺና ሴት ልጆችሽም ቀድሞ ወደ ነበራችሁበት ሁኔታ ትመለሳላችሁ:: [56]በታበይሽበት ወቅት የእኅትሽን የሰዶምን ስም ለመጥራት እንኳ ፈቃደኛ አልነበርሽም፤ [57]ይህም ኀጢአትሽ ከመገለጡ በፊት ነበር:: አሁን ግን በዙሪያሽ ሆነው ለሚንቁሽ ለኤዶም[ሐ] ሴት ልጆችና ለጎረቤቶቿ ሁሉ፣ እንዲሁም ለፍልስጥኤም ሴት ልጆች መሣለቂያ ሆነሻል:: [58]ለብልግናሽና ለአስጸያፊ ተግባርሽ የሚገባውን ቅጣት ትሸከሚያለሽ፤ ይላል *እግዚአብሔር*::

[59]“ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ቃል ኪዳኔን በማፍረስ መሐላዬን ንቀሻልና ተገቢውን ቅጣት ከእኔ ዘንድ ትቀበያለሽ:: [60]ነገር ግን በልጅነትሽ ጊዜ ከአንቺ ጋር የገባሁትን ቃል ኪዳን አስባለሁ፤ ለዘላለምም የሚኖር ቃል ኪዳን ከአንቺ ጋር እመሠርታለሁ:: [61]ከአንቺ ታላላቅ የሆኑትንና ታናናሽ የሆኑትን እኅቶችሽን ስትቀበዪ፣ አካሄድሽን ታስቢአለሽ፤ ታፍሪአለሽም:: ሴት ልጆች እንዲሆኑሽም እነርሱን ለአንቺ እሰጣለሁ፤ ከአንቺ ጋር በገባሁት ቃል ኪዳን መሠረት ግን አይደለም:: [62]ስለዚህ ከአንቺ ጋር ቃል ኪዳኔን ዐድሳለሁ፤ በዚያ ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቂአለሽ:: [63]ያደረግሽውን ሁሉ ይቅር ባልሁሽ ጊዜ፣ በደልሽ ትዝ ሲልሽ ታፍሪያለሽ፤ ከውርደትሽም የተነሣ አፍሽን ከቶ አትከፍቺም፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::’ ”

16፥40 ዮሐ8፥5፡7
16፥41 ዘዳ13፥16፤ ኤር19፥13፤ ሕዝ22፥15፤23፥10፤ 23፥27፡48
16፥42 2ሳሙ24፥25፤ ኢሳ40፥1-2፤54፥9፤ ሕዝ5፥13፤39፥29
16፥43 ዘፀ15፥24፤ መዝ78፥42፤ ሕዝ11፥21፤22፥31
16፥44 መዝ49፥4
16፥45 ቍ3፤ ኤር44፥19፤ሕዝ14፥5፤ 23፥2
16፥46 ዘፍ13፥10 -13፤ኤር3፥7፡8-11፤ ሕዝ23፥4፤ራእ11፥8
16፥47 ሕዝ5፥7
16፥48 ዘፍ15፥2፤ 19፥25፤ማቴ10፥15፤ 11፥23፡24
16፥49 ዘፍ13፥13፤ 19፥9፤መዝ138፥6፤ ኢሳ1፥10፤22፥13፤ ኤር5፥28፤ሕዝ18፥7፡ 12፡16፤28፥2፤ አሞ6፥4-6፤ ሉቃ12፥16-20፤ 16፥19፤ያዕ5፥5
16፥50 ዘፍ18፥20 -21፤19፥5፤ መዝ18፥27
16፥51 ኤር3፥8-11፤ ሕዝ5፥6-7፤23፥11
16፥52 ኤር3፥11፤ ሕዝ23፥35
16፥53 ዘዳ30፥3፤ ኢሳ19፥24-25፤ ኤር 48፥47፤ ሕዝ39፥25
16፥54 ኤር2፥26
16፥55 ሕዝ36፥11፤ ሚል3፥4
16፥57 2ነገ16፥6፤ መዝ137፥3
16፥58 ሕዝ23፥49
16፥59 ቍ8፤ ሕዝ17፥19
16፥60 ዘፍ6፥18፤ 9፥15፡16፤መዝ25፥7፤ ኤር2፥2፤ሕዝ37፥36
16፥62 ዘዳ29፥14፤ ኤር24፥7፤ሕዝ20፥ 37፡43-44፤34፥25፤ 37፥26፤ሆሴ2፥19-20
16፥63 መዝ39፥9፤ 65፥3፤78፥38፤79፥9፤ ሕዝ36፥31-32፤ ዳን 9፥7-8፤

[ሐ]57 ከብዙዎቹ የዕብራይስጥና የሱርስት የጥንት ቅጆች ጋር ተመሳሳይ ሲሆን አብዛኛዎቹ የዕብራይስጥ ቅጆች፣ ሰብዓ ሊቃናትና ቩልጌት ግን *አራም* ይላሉ

16፥40 *ያነሣሡብሻል፣ በድንጋይ ይወግሩሻል፤* ከ23፥47 ጋር ያነጻጽሩ::

16፥41 *ቤቶችሽን ያቃጥላሉ፤* የተለመደ የቅጣት ዐይነት ነው (መሳ12፥1፤ 15፥6 ይመ):: *ከእንግዲህም ለወዳጆችሽ ዋጋ አትከፍይም፤* ቍ33 ይመ::

16፥44 *ሴት ልጅ በእናቷ ትወጣለች፤* የኢየሩሳሌም ክፋት በራሷ ብቻ የሚያቆም ሳይሆን፣ ከዘር ወደ ዘር የሚተላለፍ መሆኑን የሚያመለክት ነው (ከቍ3፡45 ጋር ያነጻጽሩ)::

16፥46 *ከሴት ልጆችዋ፤* በዙሪያዋ ያሉት አነስተኛ ከተሞች ወይም የእርሷን ምግባር የሚከተሉት ሌሎች አገሮች ማለት ነው::

16፥47 *ከእነርሱ ይልቅ ፈጥነሽ ምግባረ ብልሹ ሆንሽ፤* መጽሐፍ ቅዱስ የከፋትንና የምግባረ ብልሹነትን አስከፊ ገጽታ በሚገባ ለመግለጽ፣ ብዙ ጊዜ ከተማን ወይም ሕዝብን ከሰዶም ጋር በማነጻጸር ያቀርባል (ቍ46፤ ዘዳ29፥23፤ 32፥32፤ ኢሳ1፥9 -10፤ 3፥9፤ ኤር23፥14፤ ሰቆ4፥6፤ ማቴ10፥15፤ 11፥23-24፤ ይሁ7 ይመ)::

16፥49 *የእኅትሽ የሰዶም ኀጢአት፤* በዚህ ስፍራ የተገለጸው የሚያመለክተው አመንዝራነትን ሳይሆን ከምግባር ጕድለት ይልቅ፣ ከግፍ የተነሣ የሚመጣውን በኅብረተ ሰብ ውስጥ የሚታይ ኢፍትሐዊነት ነው (ዘፍ19)::

16፥56 *በታበይሽበት ወቅት፤* ከሕዝቅኤል ዘመን በፊት የነበረውን የሚያመለክት ነው፤ ይህም ኢየሩሳሌም የእስራኤል መዲና የነበረችበትን የዳዊትንና የመጀመሪያውን የሰሎሞንን ዘመን የሚያመለክት ነው::

16፥57 *ለኤዶም ሴት ልጆች ... መሣለቂያ ሆነሻል፤* የብሉይ ኪዳን መጽሐፍ ኤዶምን በዚህ ጕዳይ ደጋግሞ ይወቅሳታል (25፥12-14፡35፤ ኢሳ 63፥1፤ አብድዩን ይመ)::

16፥59 *ቃል ኪዳኔን፤* ቍ8 እና ማብ ይመ::

16፥60 *ለዘላለም የሚኖር ቃል ኪዳን፤* 37፥26፤ ኢሳ 55፥3፤ ኤር32፥40 ይመ::

## የንስሮቹና የወይኑ ምሳሌ

**17** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ *መጣ*፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ እንቆቅልሽ አቅርብ፤ ለእስራኤልም ቤት በተምሳሌት ተናገር፤ [3]እንዲህም በል፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ትልቅ ክንፍና ረጅም ማርገብገቢያ ያለው እንዲሁም አካሉ በላባ የተሸፈነ መልኩ ዥጉርጉር የሆነ ታላቅ ንስር ወደ ሊባኖስ መጥቶ የዝግባ ዛፍ ጫፍ ያዘ፤ [4]ከጫፉም የላይኛውን ቀንበጥ ቀንጥቦ ወደ ነጋዴዎች ምድር ወሰደ፤ በሸቀጥ ነጋዴዎችም ከተማ ተከለው::

[5]“ ‘ከዚህ በኋላ ከምድሪቱ ዘር ወስዶ በመልካም ዐፈር አኖረው፤ ውሃ እንደ ልብ ባለበት ቦታ አጠገብ እንደ አኻያ ዛፍ ተከለው፤ [6]በበቀለም ጊዜ አጭርና ወደ ጐን የተንሰራፋ የወይን ተክል ሆነ፤ ቅርንጫፎቹም ወደ እርሱ አቅጣጫ ዐደጉ፤ ሥሮቹ ግን እዚያው ከበታቹ ቀሩ:: ስለዚህ የወይን ተክል ሆነ፤ ቅርንጫፎችን አወጣ፤ ለምለም ቅጠሎችንም አበቀለ::

[7]“ ‘ደግሞም ትልቅ ክንፍ ያለውና አካሉ በላባ የተሸፈነ ሌላ ታላቅ ንስር ነበር:: ያ የወይን ተክልም ውሃ ለማግኘት ከተተከለበት ቦታ ሥሩን ወደ እርሱ ሰደደ፤ ቅርንጫፉንም ወደ እርሱ ዘረጋ:: [8]ቅርንጫፍ እንዲያወጣ፣ ፍሬ እንዲያፈራና ያማረ የወይን ተክል እንዲሆን በአጠገቡ ብዙ ውሃ ባለበት በመልካም መሬት ተተክሎ ነበር::”

[9]“እንዲህም በላቸው፣ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ያድግ ይሆን? ይጠወልግ ዘንድ ሥሩ ተነቅሎ ፍሬው አይረገፍምን? ቀንበጡም ሁሉ ይደርቃል:: ከሥሩ ለመንቀል ብርቱ ክንድና የብዙ ሰው ጕልበት አያስፈልገውም:: [10]በሌላ ስፍራ ቢተከልስ ይጸድቅ ይሆን? የምሥራቅ ነፋስ ሲመታውስ ባደገበት ስፍራ ፈጽሞ አይደርቅምን?’ ”

[11]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ *መጣ*፤ [12]“ለዚህ ዐመፀኛ ቤት እንዲህ በል፤ ‘የእነዚህ ነገሮች ትርጕም ምን እንደ ሆነ አታውቁምን?’ እንዲህ በላቸው፣ ‘የባቢሎን ንጉሥ ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ፤ ንጉሥዋንና መሳፍንቷን ማረከ፤ ወደ ባቢሎንም ይዞአቸው ተመለሰ:: [13]ከንጉሣውያን ቤተ ሰብ አንዱን ወስዶ ከእርሱ ጋር ውል አደረገ፤ በመሐላም ቃል አስገባው፤ የምድሪቱንም ታላላቅ ሰዎች ማርኮ ወሰደ፤ [14]ይኸውም የምድሪቱ መንግሥት ተዋርዳ የእርሱን ውል በመጠበቅ ብቻ እንድትኖር እንጂ፣ ዳግመኛ እንዳታንሰራራ ለማድረግ ነበር:: [15]ንጉሡ ግን በእርሱ ላይ ዐመፀ፤ ፈረሶችና ብዙ ሰራዊት ለማግኘት መልእክተኞችን ወደ ግብፅ ላከ፤ ይሳካለት ይሆን? እንዲህ ዐይነቱን ነገር የፈጸመ ያመልጣልን? ውል ያፈረሰስ ሳይቀጣ ይቀራልን?

[16]“ ‘በሕያውነቴ እምላለሁ! ይላል ልዑል *እግዚአብሔር*፤ መሐላውን ባቀለለበት፣ ውሉን ባፈረሰበት፣ በዙፋንም ላይ ባስቀመጠው ንጉሥ ምድር በባቢሎን ይሞታል:: [17]በባቢሎናውያን ብዙ ሕይወት ለማጥፋት በከተማዋ ዙሪያ ዐፈር በሚደለድሉበትና ምሽግ በሚሠሩበት ጊዜ፣ ፈርዖን ከኀያል ሰራዊቱና ከብዙ ጭፍሮቹ ጋር በጦርነት ሊረዳው አይችልም:: [18]ያደረገውን መሐላ በማቃለልና እጁን ያስገባበትን ውል በማፍረስ ይህን ሁሉ ስለ ፈጸመ ከቅጣት አያመልጥም::

[19]“ ‘ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በሕያውነቴ እምላለሁ! ያቃለለውን መሐላዬንና ያፈረሰውን ኪዳኔን በራሱ ላይ አመጣለሁ:: [20]*መረቤን* በላዩ እዘረጋለሁ፤ በወጥመዴም ይያዛል:: ወደ ባቢሎን እወስደዋለሁ፤ በእኔ ላይ ስላመፀም በዚያ እፈርድበታለሁ:: [21]የሚሸሸው ወታደሩ ሁሉ በሰይፍ ይወድቃል፤ የተረፉትም ወደ ነፋስ ይበተናሉ፤ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ተናገርሁ ታውቃላችሁ::

[22]“ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “ከረጅሙ ዝግባ ጫፍ እኔው ራሴ ቀንበጡን ወስጄ እተክለዋለሁ፤ ከቀንበጦቹ ጫፍ አንዱን ቀንጥቤ ከሁሉ ከፍ ባለው

ሮሜ3+19
17+2 መሳ14+2፤ ሕዝ20+49
17+3 ዘዳ28+49፤ ኤር22+23፤49+22፤ ዳን7+4፤ሆሴ8+1
17+4 ኢሳ10+33
17+5 ዘዳ8+7-9፤ መዝ1+3፤ኢሳ44+4፤ ሕዝ31+5
17+6 ኢዮ5+3፤ ኢሳ18+5
17+7 ሕዝ31+4
17+8 ኢዮ18+19፤ ሚል4+1
17+9 ኤር42+10፤ አሞ2+9
17+10 ኢዮ1+19፤ ሕዝ15+4፤ሆሴ12+11 13+15
17+12 ዘዳ21+10፤ 2ነገ24+15፤ 2ዜና36+10፤ ሕዝ12+9፤24+19
17+13 ዘፀ23+32፤ 2ዜና36+13፤ ኢሳ3+2፤ኤር37+1
17+14 ሕዝ29+14
17+15 ዘዳ17+16፤ መዝ56+7፤ ኢሳ30+2፡5፤ኤር34+3፤ 37+5፤38+18፤52+3፤ ሕዝ29+16
17+16 2ነገ24+17፤ ኤር52+11፤ ሕዝ12+13
17+17 ኢሳ36+6፤ ኤር37+5፡7፤ ሕዝ4+2፤29+6-7
17+18 2ነገ10+15፤ 1ዜና29+24
17+19 ኤር7+9፤ ሕዝ16+59፤21+23፤ ሆሴ10+4
17+20 ኤር2+35፤ ሕዝ12+13፤15+8
17+21 ዘሌ26+33፤ 2ነገ25+5፡11፤ ኤር27+8፤ ሕዝ12+14፤ዘካ2+6
17+22 ቍ23፤ 2ነገ19+30፤ኢሳ2+2፤ 4+2፤ኤር23+5፤ ሕዝ 20+40፤36+1፤ 37+22፤40+2፤

17+2 *እንቆቅልሽ ... በተምሳሌት ተናገር፤* እንቆቅልሹ ከቍ3-10 የተጠቀሰው ሲሆን፣ ፍቺው ደግሞ ከቍ11-21 ላይ ተሰጥቶአል::

17+3 *ታላቅ ንስር፤* ናቡከደነፆርን ነው (ቍ12 ይመ):: *ሊባኖስ፤* ኢየሩሳሌምን ማለት ነው (ቍ12 ይመ):: *የዝግባ፤* የዳዊትን ሥርወ መንግሥትና ንጉሣዊውን ቤተ ሰብ የሚያመለክት ነው::

17+4 *ቀንበጥ፤* ዮአኪንን ማለት ነው:: *ወደ ነጋዴዎች ምድር፤* የባቢሎን ምድር ነው (ቍ12፤ 16+29 ይመ):: *በነጋዴዎችም ከተማ፤* የባቢሎን ከተማ ነው::

17+5 *ዘር፤* የኢዮስያስን ልጅ ሴዴቅያስን ነው፤ እርሱም የኢዮአካዝና የኢዮአቄም ወንድም፣ እንዲሁም የዮአኪን አጎት ነው (2ነገ23-24 ይመ):: *ተከለው፤* አነገሠው ማለት ነው (2ነገ 24+17)::

17+6 *አጭርና ወደ ጐን የተንሰራፋ የወይን ተክል፤* በብዙ ሺህ የሚቈጠሩ ዋና ዋናዎቹ የይሁዳ ሰዎች በምርኮ ስለ ተወሰዱ፣ ከእንግዲህ ቁመተ ረጅም ዝግባ አይኖርም (2ነገ 24+15-16 ይመ፤ እንዲሁም ኤር52+28 ይመ):: ሆኖም የ15+2 ማብ ይመ::

17+7 *ሌላ ታላቅ ንስር፤* የግብፁ ፈርዖን ነው፤ ይህም ዳግማዊ ሳሜቲክስ (ከ595-589 ዓ.ቅ.ክ.) ወይም ሖፍራ (589-570 ዓ.ቅ.ክ.) ሊሆን ይችላል:: በኤር44+30 ላይ የተጠቀሰው ሖፍራ በ586 ዓ. ቅ.ክ. ኢየሩሳሌምን የረዳው ፈርዖን ሊሆን ይችላል (ኤር 37+5 ይመ):: በም8 (592 ዓ.ቅ.ክ.) እና በም20 (591 ዓ.ቅ.ክ.) መካከል የገባው ቅደም ተከተሉን የዘመን አቈጣጠር ጠብቆ ከሆነ፣ ስሙ የተጠቀሰው ፈረዖን ዳግማዊ ሳሜቲክስ መሆን አለበት:: *ሥሩን ወደ እርሱ ሰደደ፤* በናቡከደነፆር ላይ በማመፅ (2ነገ24+20 ይመ)፣ ሴዴቅያስ ወታደራዊ ድጋፍ ለማግኘት (ቍ15) መልእክተኞችን ወደ ግብፅ ላከ::

17+10 *የምሥራቅ ነፋስ፤* ሰብል የሚያደርቅ (19+12 ይመ)፣ ካምሲን በመባል የሚታወቅ ሞቃትና ደረቅ አየር ነው:: በዚህ ስፍራ የሚያመለክተው ናቡከደነፆርንና ባቢሎናውያንን ሰራዊቱን ነው::

17+12 *ለዚህ ዐመፀኛ ቤት፤* 2+3 እና ማብ ይመ::

17+15 *ያመልጣልን? ውል ያፈረሰ ሳይቀጣ ይቀራልን?* የምዕራፉ ዐቢይ ሐሳብ ነው (ቍ16:18 ይመ)::

17+16 *በባቢሎን ይሞታል፤* 2ነገ25+7 ይመ::

17+19 *መሐላዬንና ያፈረሰውን ኪዳኔን፤* የይሁዳ ንጉሥ በእግዚአብሔር ስም የገባውን መሐላና ኪዳን መጠበቅ ነበረበት፤ ታማኝነትን ማፍረስ እግዚአብሔርን እንደመናቅ ይቈጠራል::

ተራራ ላይ እተክለዋለሁ:: [23]ከፍ ባለው የእስራኤል ተራራ ላይ እተክለዋለሁ፤ ቅርንጫፎች ያወጣል፤ ፍሬ ያፈራል፤ ያማረም ዝግባ ይሆናል:: የወፍ ዐይነት ሁሉ መኖሪያውን በዚያ ያደርጋል፤ በቅርንጫፎቹም ጥላ ሥር ያርፋል:: [24]የዱር ዛፎች ሁሉ ረጅሙን ዛፍ ዝቅ ዝቅ ያለውንም ዛፍ፣ ከፍ የማደርግ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ፤ የለመለመውን ዛፍ አደርቃለሁ፤ ደረቁንም አለመልማለሁ::"

"'እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ፤ እኔው አደርገዋለሁ::' "

## ኀጢአት የምትሠራ ነፍስ ትሞታለች

**18** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"ስለ እስራኤል ምድር፣

" 'አባቶች ጐምዛዛ የወይን ፍሬ በሉ፤
 የልጆችንም ጥርስ አጠረሰ' እያላችሁ የምትመስሉት ተምሳሌት ምን ለማለት ነው?

[3]"ቢሕያወቴ እምላለሁ! ይላል ልዑል እግዚአብሔር፤ ከእንግዲህ ይህን ምሳሌ በእስራኤል ምድር አትመስሉም:: [4]እነሆ ነፍስ ሁሉ የእኔ ናት፤ የአባት ነፍስ የእኔ እንደ ሆነች ሁሉ የልጁም ነፍስ የእኔ ናት፤ ኀጢአት የምትሠራ ነፍስ እርሷ ትሞታለች::

[5]"በቅንነትና በትክክል የሚሠራ፣
 ጻድቅ ሰው ቢገኝ፣
[6]በኰረብታ ባሉ አብያተ ጣዖት የቀረበውን
 አይበላም፤
 በእስራኤል ቤት ወዳሉት ጣዖታት
 አይመለከትም
የባልንጀራውን ሚስት አያባልግም፤
 ከሴት ጋር በወር አበባዋ ጊዜ
 አይተኛም::
[7]ማንንም አይጨቍንም፤
 ነገር ግን በመያዣ የወሰደውን እንኳ
 ለተበዳሪው ይመልሳል፤
ለተራብ የራሱን እንጀራ፣
 ለተራቈተም ልብስ ይሰጣል እንጂ
 በጕልበት አይቀማም::
[8]በዐራጣ አያበድርም፣
 ከፍተኛ ወለድም አይቀበልም[T]::
እጁን ከበደል ይሰበስባል፤
 በሰውና በሰው መካከል በትክክል
 ይፈርዳል::
[9]ሥርዐቴን ይከተላል፤
 ሕጌንም በቅንነት ይጠብቃል::
ይህ ሰው ጻድቅ ነው፤
 ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል፤
 ይላል ጌታ እግዚአብሔር::

[10]"ነገር ግን ይህ ሰው ደም የሚያፈስ ወይም ከሚከተሉት ኀጢአቶች ማንኛውንም[ሀ] የሚፈጽም ዐመፀኛ ልጅ ቢኖረው፣

43+12
17+23 ቍ22፤ መዝ92+12፤ ኢሳ2+2፤27+6፤ ኤር31+12፤ ሕዝ31+6፤ዳን4+12፤ ሆሴ14+5-7፤ ማቴ13+32
17+24 ዘኍ17+8፤ 1ሳሙ2+7-8፤ መዝ52+5፤96+12፤ ኢሳ2+13፤27+6፤ ዳን5+21፤ሕዝ19+12፤ 21+26፤22+14፤ 37+13፤አሞ9+11
18+2 ኢዮ21+19፤ ኢሳ3+15፤ኤር31+29
18+3 መዝ49+4
18+4 ቍ20፤ ዘፍ18+23፤ ዘፀ17+14፤ 2ነገ14+6፤ኢዮ21+20፤ ምሳ13+21፤ ኢሳ42+5፤ሕዝ33+8፤ ሮሜ6+23
18+6 ዘሌ12+2፤ 15+24፤ዘዳ4+19፤ ሕዝ6+2:13፤20+24፤ አሞ5+26
18+7 ዘፀ20+15፤ 22+21:26፤ ዘዳ15+11፤ኢዮ22+7፤ ሕዝ16+49፤ሚል3+5፤ ማቴ25+36፤ ሉቃ3+11፤ያዕ5+4
18+8 ዘፀ18+21፤ 22+25፤ዘሌ25+35-37፤ዘዳ23+19-20፤ ኤር22+3፤ዘካ8+16
18+9 ዘሌ18+5፤ 19+37፤ሕዝ11+12፤ 20+11፤አሞ5+4፤ዕን2+4
18+10 ዘፀ21+12፤ሕዝ22+6

[T]8 ወይም *ወለድ አይወስድም፤* እንዲሁም በቍ13 እና 17
[ሀ]10 ወይም *ማናቸውንም በወንድሙ ላይ*

17+22 *ዝግባ፤* የቍ3 ማብ ይመ:: *እኔው ራሴ፤* አዲስ በሆነ መንገድ የቀረበ ደስ የሚያሰኝ መሲሐዊ ተስፋ ነው:: *ቀንበጦቹ፤* የዳዊትን ቤተ ሰብ የሚመለከት ነው (ከኢሳ11+1፤ ዘካ3+8፤ 6+12 ጋር ያነጻጽሩ):: *እተክለዋለሁ፤* አነግሠዋለሁ ማለት ነው (ቍ5 ይመ):: *ከሁሉ ከፍ ባለው ተራራ ላይ፤* ኢየሩሳሌምን ማለት ነው::

17+23 *ወፍ ... መኖሪያውን በዚያ ያደርጋል፤* ማር4+32 ይመ::

*18+2 ስለ እስራኤል ምድር፤* ችግሩን የቀመሱት ሰዎች የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ ምን እንደሚሆን የተነገረ ነው:: *አባቶች ... አጠረሰ፤* ተምሳሌቱ ስለ ራስ ማዘንን፣ ዕድለ ቢስ መሆንን፣ ተስፋ መቍረጥንና በእግዚአብሔር ፍትሕ ላይ የሚያፌዝ ቢመስልም፣ በእስራኤላውያን መሠረታዊ እምነት ላይ ተመሥርቶ የተነገረ ነው (ዘፀ20+5፤ 34+7 ይመ፤ ሕዝቅኤልም በም16 እና 23 ላይ የተናገረውን ይመ)፤ በሰቆ5+7 ላይ እንደ እውነተኛ ንስሐ ተገልጾአል:: *አጠረሰ፤* በዕብራይስጥ፣ "አደነዘዘ" ወይም "አበላሸ" ማለት ሲሆን (ከመክ10+10 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ምናልባት መራራ ወይም ጐምዛዛ ነገር ከተበላ በኋላ በምላስ ላይ የሚሰማውን ስሜት የሚገልጽ ሊሆን ይችላል:: *ተምሳሌት፤* ከኤር31+29 ጋር ያነጻጽሩ፤ ተምሳሌቱ በመጀመሪያ የተነገረው በኢየሩሳሌም ነው:: ኤርምያስ ተምሳሌቱ እንደአከተመለት ሲያወሳ፣ ሕዝቅኤል ደግሞ መጨረሻው እንደ ተቃረበ ይናገራል::

18+3 *እኔ ሕያው እግዚአብሔርን፤ በራሴ እምላለሁ፤* የማይለወጠውን የእግዚአብሔርን ሐሳብ የሚገልጽ መለኮታዊ መሐላ ሲሆን፤ በሕዝቅኤል መጽሐፍም ተደጋግሞ ተጠቅሶአል (5+11፤ 14+16:18:20፤ 16+48፤ 17+16:19፤ 20+3:31:33፤ 33+11:27፤ 34+8፤ 35+6:11 ይመ)::

18+4 *ኀጢአት የምትሠራ ነፍስ እርሷ ትሞታለች፤* ከአባት ወደ ልጅ ስለሚተላለፍ በደል፣ በዘፀ 20+5፤ 34+7 ላይ የተናገረውን ሕዝቡ በትክክል ስላልተረዳው፣ ሕዝቅኤል ይህንኑ አስመልክቶ በመቀጠል ድምፁን ከፍ አድርጎ የተናገረው ነው:: ወይም ኀጢአት አለመኖሩን ለመግለጽ የተናገረው መሠረታዊ ትምህርት ይሆናል:: *ነፍስ፤* ሕይወትን ወይም አንድን ሰው ለመግለጽ የገባ እንጂ መንፈስ ከሥጋ ጋር ያለውን ግንኙነትና ልዩነት ለመግለጽ የገባ አይደለም::

18+5 *ጻድቅ ሰው፤* ሕግን የሚጠብቅ የመጀመሪያ ትውልድ ማለት ነው:: በዝርዝር ተከታዮቹ የተጠቀሱት ዐሥራ አምስቱ ትእዛዛት ከፊሉ ሃይማኖታዊ ሥርዐትን የሚመለከቱ ሲሆኑ፣ አብዛኞዎቹ ግብረ ገብነትን የሚመለከቱ ናቸው:: በዘፀ20 እና በዘዳ 5 ያሉትን ዐሥርቱን ትእዛዛት ይመ፤ ከመዝ15+2-5፤ 24+3-6፤ ኢሳ33+15 ጋር ያነጻጽሩ::

18+6 *በኰረብታ ባሉ አብያተ ጣዖት፤* በኰረብታ ማምለኪያ ስፍራዎች ላይ ለጣዖት የተሠዋን ሥጋ መብላትን የሚመለከት ነው (6+3፤ ሆሴ4+13 ይመ):: *አይመለከትም፤* እርዳታን ለማግኘት አይፈልግም ማለት ነው (23+27፤ 33+25፤ መዝ121+1 ይመ):: *ጣዖታት፤* የ6+4 ማብ ይመ:: *አያባልግም፤* ዘፀ20+14፤ ዘዳ22+22፤ ዘሌ18+20፤ 20+10 ይመ:: በወር አበባዋ ጊዜ ከሴት ጋር መተኛት እንደማይገባ በዘሌ15+19-24፤ 18+19፤ 20+18 ተጽፎ ይገኛል፤ ይህ ሐሳብ ግን በቍ11:15 ላይ ተጠቅሶ አይገኝም::

18+7 *አይጨቍንም፤* ባለጠጎች ከድኾች ጥቅም የሚያገኙበትን ሁኔታ ይገልጻል:: *በመያዣ የወሰደውን እንኳ ለተበዳሪው ይመልሳል፤* ዘፀ22+26፤ ዘዳ24+12-13፤ አሞ2+8 ይመ:: *አይቀማም፤* ስርቆትን በተመለከተ በዘፀ20+15፤ ዘዳ5+1 ላይ የተጻፈውን ይመ:: በስውር ወይም በማጭበርበር ሳይሆን በጕልበትና በመሣሪያ በማስፈራራት የሚደረገውን ቅሚያ ነው (ዘሌ19+13 ይመ):: *ለተራብ የራሱን እንጀራ፤* ዘዳ15+7-11፤ ማቴ25+31-46 ይመ::

18+8 *በዐራጣ አያበድርም፤* 22+12፤ መዝ15+5፤ ምሳ28+8 ይመ:: በዘፀ22+25፤ ዘሌ25+35-37፤ ዘዳ23+19 ላይ እንደ ተጻፈው፣ ለተቸገረ በዐራጣ ማበደር በጥብቅ የተከለከለ ነው:: በዘዳ23+20 ላይ እስራኤላዊ ለመጻተኛ ወይም ለእንግዳ በወለድ ማበደር እንደሚችል ተገልጾአል፤ በዚህ ስፍራ ሕዝቅኤል የሚከለክለው፣ ከሚገባ በላይ ወለድ መጠየቅን ነው:: ባንክ የሚሰጠው ዘመናዊ የብድር አሰጣጥና ወለድ አከፋፈል ግን ከዚህ ጋር ግንኙነት የለውም::

18+9 *ይህ ሰው ጻድቅ ነው፤ ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል፤* ትእዛዛትን እንደጠበቀ ከተጣራ በኋላ፣ የፍርድ ውሳኔ ይሰጣል (ከመዝ15+5፤ 24+5 ጋር ያነጻጽሩ):: *ይኖራል፤* የ16+6 ማብ ይመ፤ በሕይወት መኖርን ብቻ ሲሆን፣ ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት ማድረግን ያመለክታል (መዝ63+3፤ 73+27-28 ይመ)::

18+10 *ዐመፀኛ ልጅ፤* ክፉ የሆነ ትውልድ ማለት ነው፤ ቀደም ብለው የተጠቀሱት ትእዛዛት ገሚሶች (ስምንቱ) በተከታዩ ተገልጸዋል፤ ይሁን እንጂ፣ የተዘረዘሩት ለየት ባለ መንገድ ነው::

[11]አባትየው አንዱንም ባያደርግ፣

“ልጁ ግን በኰረብታ መስገጃ የቀረበውን
 ቢበላ፣
 የባልንጀራውን ሚስት ቢያባልግ፣
[12]ድኻውንና ችግረኛውን ቢጨቍን፣
 በጕልበት ቢቀማ፣
በመያዣነት የወሰደውን ባይመልስ፣
 ወደ ጣዖታት ቢመለከት፣
 አስጸያፊ ተግባራትን ቢፈጽም፣
[13]በዐራጣ ቢያበድር፣
 ከፍተኛ ወለድም ቢቀበል፣

እንዲህ ዐይነቱ ሰው በሕይወት ይኖራልን? ከቶ አይኖርም! እነዚህን አስጸያፊ ነገሮች አድርጓልና በእርግጥ ይሞታል፤ ደሙም በገዛ ራሱ ላይ ይሆናል።

[14]“ይህም ልጅ ደግሞ በተራው ልጅ ቢወልድና ልጁም አባቱ ያደረገውን ኀጢአት ሁሉ አይቶ ባይፈጽም፣ ይኸውም፦

[15]በኰረብታ መስገጃ የቀረበውን ባይበላ፣
 በእስራኤል ቤት ወዳሉት ጣዖታት
 ባይመለከት፣
 የባልንጀራውን ሚስት ባያባልግ፣
[16]ሰውን ባይጨቍን፣
 ብድር ለመስጠት መያዣ ባይጠይቅ፣
 በጕልበቱ ባይቀማ፣
 ነገር ግን ምግቡን ለተራበ፣
 ልብሱን ለተራቈተ ቢሰጥ፣
[17]እጁን ድኻን ከመበደል ቢሰበስብ፣
 ዐራጣ ወይም ከፍተኛ ወለድ ባይቀበል፣
 ሕጌን ቢጠብቅ፣ ሥርዐቴንም ቢከተል፣

በሕይወት ይኖራል እንጂ በአባቱ ኀጢአት አይሞትም። [18]አባቱ ግን የሰውን መብት ስለ ደፈረ፣ ወንድሙን በጕልበት ስለ ቀማና በሕዝቡ መካከል የማይገባውን ስላደረገ በገዛ ኀጢአቱ ይሞታል።

[19]“እናንተ ግን፣ ‘ልጅ ስለ አባቱ ኀጢአት ለምን አይቀጣም?’ ትላላችሁ። ልጁ ቀናና ትክክለኛውን ነገር ስላደረገ፣ ሥርዐቴንም ሁሉ በጥንቃቄ ስለ ጠበቀ በሕይወት ይኖራል። [20]መሞት የሚገባት፣ ኀጢአት የሠራችው ነፍስ ናት። ልጅ በአባቱ ኀጢአት አይቀጣም፤ አባትም በልጁ ኀጢአት አይቀጣም። ጻድቁ የጽድቁን ፍሬ ያገኛል፤ ኀጢአተኛውም የኀጢአቱን ዋጋ ይቀበላል።

[21]“ኀጢአተኛ ከሠራው ኀጢአት ሁሉ ተመልሶ ሥርዐቴን ሁሉ ቢጠብቅ፣ ቀናና ትክክለኛውን ነገር ቢያደርግ ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል እንጂ አይሞትም። [22]በደሉ ሁሉ አይታሰብበትም፤ በጽድቅ መንገድ ሄዷልና በሕይወት ይኖራል። [23]በውኑ ኀጢአተኛ ሲሞት ደስ ይለኛልን? ይላል ጌታ እግዚአብሔር። ይልቁን ከመንገዱ ተመልሶ በሕይወት ሲኖር ደስ አይለኝምን?

[24]“ጻድቅ ሰው ግን ከጽድቁ ተመልሶ ኀጢአት ቢሠራ፣ ኀጢአተኛው የሚያደርገውንም አስጸያፊ ነገር ቢፈጽም፤ ይህ ሰው በውኑ በሕይወት ይኖራልን? ከሠራው ጽድቅ አንዱም አይታሰብለትም፤ ታማኝ ባለመሆኑና ከፈጸመው ኀጢአት የተነሣ ይሞታል።

[25]“እናንተ ግን፣ ‘የጌታ መንገድ ቀና አይደለችም’ ትላላችሁ። የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ስማ፤ መንገዴ ቀና አይደለችምን? ቀና ያልሆነውስ የእናንተ መንገድ አይደለምን? [26]ጻድቅ ከጽድቁ ተመልሶ ኀጢአት ቢሠራ በኀጢአቱ ይሞታል፤ ከፈጸመውም በደል የተነሣ በሕይወት አይኖርም። [27]ኀጢአተኛው ግን ከክፉ ሥራው ተመልሶ በታማኝነትና በቅንነት ቢኖር ሕይወቱን ያድናል። [28]የፈጸመውን በደል ሁሉ ተገንዝቦ ካደረገው ክፋት ሁሉ ስለ ተመለሰ፣ ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል እንጂ አይሞትም። [29]የእስራኤል ቤት ግን፣ ‘የጌታ መንገድ ቀና አይደለችም’ ይላል። የእስራኤል ቤት ሆይ! መንገዴ ቀና አይደለችምን? ቀና ያልሆነችውስ የእናንተ መንገድ አይደለችምን?

[30]“የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ስለዚህ እንደየሥራችሁ በእያንዳንዳችሁ ላይ እፈርዳለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር። እንግዲህ ንስሓ ግቡ! በኀጢአት እንዳትጠፉ፣ ከኀጢአታችሁ ሁሉ ተመለሱ። [31]በእኔ ላይ የፈጸማችሁትን በደል ሁሉ ወደ ኋላ ጣሉት፤ አዲስ ልብና አዲስ መንፈስ ይኑራችሁ። የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ለምን ትሞታላችሁ? [32]ማንም እንዲሞት አልሻምና፣ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ ወደ እኔ ተመለሱና በሕይወት ኑሩ!

## ስለ እስራኤል መሳፍንት የወጣ ሙሾ

**19** “ስለ እስራኤል መሳፍንት ሙሾ አውጣ፤ [2]እንዲህም በል፤

18፥11 ሕዝ22፥9
18፥12 ዘፀ22፥22-27፤2ነገ21፥11፤ ኢዮ 24፥9፤ ኢሳ59፥6-7፤ ኤር22፥17፤ ሕዝ16፥49፤አሞ4፥1፤ ዕን2፥6
18፥13 ዘፀ22፥25፤ ዘሌ20፥9፤ሕዝ33፥4-5፤ሆሴ12፥14
18፥14 2ዜና34፥21፤ ምሳ23፥24
18፥15 መዝ24፥4፤ ሕዝ22፥9
18፥16 ዘፀ22፥27፤ መዝ41፥1፤ኢሳ58፥7፡10፤ሕዝ16፥49
18፥17 መዝ1፥2
18፥19 ዘፀ20፥5፤ ዘዳ5፥9፤ኤር15፥4፤ ዘካ1፥3-6
18፥20 ዘኍ15፥31፤ዘዳ24፥16፤ 1ነገ8፥32፤2ነገ14፥6፤ ኢሳ3፥11፤ሕዝ7፥27፤ 14፥14፤ማቴ16፥27፤ ዮሐ9፥2
18፥21 ዘፍ26፥5፤ ኤር18፥8፤ ሕዝ13፥22፤36፥27
18፥22 መዝ18፥20-24፤ኢሳ43፥25፤ ዳን4፥27፤ሚክ7፥19
18፥23 ኢዮ37፥23፤ መዝ147፥11፤ ሰቆ3፥33፤ሕዝ16፥6፤ ሚክ7፥18፤1ጢሞ2፥4
18፥24 1ሳሙ15፥11፤ 2ዜና24፥17-20፤ ኢዮ35፥8፤ምሳ21፥16፤ ኤር34፥16፤ሕዝ3፥20፤ 20፥27፤2ጴጥ2፥20-22
18፥25 ዘፍ18፥25፤ ኤር2፥29፤12፥1፤ ሕዝ33፥17፤ሶፎ3፥5፤ ሚል2፥17፤3፥13-15
18፥27 ኢሳ1፥18፤ ሕዝ13፥22
18፥28 ኢሳ55፥7
18፥30 ኢሳ1፥27፤ ኤር35፥15፤ሕዝ7፥3፤ 24፥14፤33፥20፤ ሆሴ12፥6፤ማቴ3፥2፤ 1ጴጥ1፥17
18፥31 መሳ6፥8፤ መዝ51፥10፤ ኢሳ1፥16-17፤ ኤር27፥13፤ ሕዝ11፥19፤36፥26
18፥32 2ዜና7፥14፤ ኢዮ22፥23፤37፥23፤ ኢሳ55፥7፤ሕዝ16፥6፤ ሚል3፥7
19፥1 ቍ14፤2ነገ 24፥6፤ኤር7፥29፤9፥10፡20፤ሕዝ26፥17፤ 27፥2፡32፤28፥12፤ 32፥2፡16፤አሞ5፥1

18፥13 *ደሙም በገዛ ራሱ ላይ ይሆናል፤* ስለ ፈጸመው ኀጢአት ተጠያቂ ይሆናል ማለት ነው (ዘሌ20፥9፡11-12፡ 16፡27ይመ)።

18፥14 *ልጁም፤* ጻድቅ የሆነ የልጅ ልጅ ማለት ነው፤ ዐሥራ ሁለቱ ትእዛዛት ቀርበዋል።

18፥21 *ኀጢአተኛ ... ተመልሶ ... ቢጠብቅ ... በሕይወት ይኖራል፤* ከቍ1-20 ያለው ከአባት ወደ ልጅ ተያይዞ የመጣው የበደል ሰንሰለት ሊደመሰስ እንደሚችል ሲያመለክት ከቍ21-29 ያለው ደግሞ በሰው ሕይወት ውስጥ የሚገኘው ከፍተኛ የበደለኝነት ስሜት ድል እንደሚነሣ ያስተምራል።

18፥24 *ጻድቅ ሰው ... ተመልሶ፤* ዐውቀውና ወደው ከጽድቅ መንገድ ለሚመለሱ በዕብ2፥3፤ 2ጴጥ2፥20-22 ላይ ማስጠንቀቂያ ተሰጥቶአቸዋል።

18፥26 *ጻድቅ፤* ከቍ26-29 ባለው ውስጥ፣ ከቍ21-25 ላይ የተነሣውን የመከራከሪያ ሐሳብ በድጋሚ ተጠቅሶአል።

18፥30 *ስለዚህ፤* እስከ አሁን ለቀረበው ንግር መደምደሚያ ሐሳብ ነው። *በእያንዳንዳችሁ፤* በደለኛ የሆነው መላው የእስራኤል ቤት ቢሆንም፣ ትክክለኛ የሆነው የእግዚአብሔር ፍርድ ግን፣ እያንዳንዱን ግለሰብ ይመለከተዋል። *ንስሓ ግቡ፤* ለንስሓ የተደረገ ዳግመኛ ጥሪ ነው (14፥6 ይመ)።

18፥31 *አዲስ ልብ ... ይኑራችሁ፤* ያለ አንዳች ቅድመ ሁኔታ ተሰጥቶ የነበረው የተስፋ ቃል (11፥9፤ 36፥26)፣ እዚህ ላይ ግን ሊጨበጥ እንደሚቻል ተገልጸአል (በፊል2፥12 እና 2፥13 ላይ ከተጠቀሰው ተመሳሳይ ሐሳብ ጋር ያነጻጽሩ)።

18፥32 *አልሻምና፤* ቍ23 ላይ የተነገረው በዚህ የመጨረሻው ማጠቃለያ ተንጸባርቆአል፤ ይህንንም አንዳንዶች የሕዝቅኤል መጽሐፍ ዋና መሆኑን ይገልጻሉ።

19፥1 *መሳፍንት፤* ነገሥታትን ማለት ነው። *ሙሾ፤* በ2ሳሙ 1፥17-27 እንደተጻፈው ለሞቱ መሪ ዎች በቀብር ሥነ ሥርዐት ላይ

"'እናትህ በአንበሶች መካከል እንዴት
ያለች አንበሳ ነበረች!
በደቦል አንበሶች መካከል ተጋደመች፤
ግልገሎቿንም በዚያ አሳደገች።
3ከግልገሎቿ መካከል አንዱን አሳደገችው፤
እርሱም ብርቱ አንበሳ ሆነ።
ግዳይ መንጠቅን ተማረ፤
ሰዎችንም በላ።
4አሕዛብም ስለ እርሱ ሰሙ፤
በጕድጓዳቸውም ገብቶ ተያዘ፤
እነርሱም በሰናግ ጐተተው፣
ወደ ግብፅ ምድር ወሰዱት።

5"'ተስፋዋ መጨናገፉን፣
የጠበቀችውም አለመሳካቱን ባየች ጊዜ፣
ከግልገሎቿ ሌላውን ወስዳ፣
ብርቱ አንበሳ አድርጋ አሳደገችው።
6እርሱም በአንበሶች መካከል ተጐማለለ፤
እየበረታም ሄደ፤
ግዳይ መንጠቅን ተማረ
ሰዎችንም በላ።
7ምሽጎቻቸውን አወደመ፤[ሰ]
ከተሞቻቸውንም ባድማ አደረገ፤
ምድሪቷና በውስጧ ያሉት ሁሉ፣
ከግሣቱ የተነሣ ተንቀጠቀጡ።
8በዙሪያው ያሉ አሕዛብ ተነሡበት፤
ከየአገሩም ሁሉ ተሰበሰቡበት፤
መረባቸውን ዘረጉበት፤
በጕድጓዳቸውም ገብቶ ተያዘ።
9በሰናግም በመጐተት ቀፎ ውስጥ ከተው፤
ወደ ባቢሎን ንጉሥ አመጡት፤
ድምፁ በእስራኤል ተራሮች ላይ፣ ዳግመኛ
እንዳይሰማ፣
በእስር ቤት አኖሩት።

10"'እናትህ በውሃ አጠገብ የተተከለ፣
በዕርሻ ውስጥ ያለ፣[ሐ]
ከውሃም ብዛት የተነሣ፣
ያፈራና የተንሰራፋ የወይን ተክል
መሰለች።
11ቅርንጫፎቿ ለበትረ መንግሥት
የሚሆኑ፣ ጠንካሮች ነበሩ፤
ጥቅጥቅ ባሉ ቅጠሎች መካከል፣
በቁመቷና በብዙ ቅርንጫፎቿ፣
ዘለግ ብላ፣ ጐልታ ትታይ ነበር።
12ነገር ግን በቍጣ ተነቀለች፤
ወደ ምድርም ተጣለች።
የምሥራቅ ነፋስ አደረቃት፤
ፍሬዎቿንም አረገፈባት።
ብርቱዎቹ ቅርንጫፎቿ ክው አሉ፤
እሳትም በላቸው።
13አሁን ውሃ በተጠማ ደረቅ ምድር፣
በበረሓ ውስጥ ተተከለች።
14ከዋና ቅርንጫፎቿ[መ] ከአንዱ እሳት ወጣ፤
ፍሬዋንም በላ።
በትረ መንግሥት የሚሆን፣
አንድም ጠንካራ ቅርንጫፍ
አልተረፈም።'

ይህ ሙሾ ነው፤ ለሐዘን እንጕርጕሮም ይሆ
ናል።"

## ዐመፀኛዪቱ እስራኤል

**20** በሰባተኛው ዓመት፣ በአምስተኛው ወር፣ ከወሩም በዐሥረኛው ቀን ከእስራኤል ሽማግሌዎች አንዳንዶቹ *የእግዚአብሔርን ሐሳብ* ሊጠይቁ መጡ፤ በፊቴም ተቀመጡ።

2*የእግዚአብሔርም* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 3"የሰው ልጅ ሆይ፤ ለእስራኤል ሽማግሌዎች እንዲህ ብለህ ንገራቸው፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ሐሳቤን ልትጠይቁ መጣችሁን? በሕያውነቴ እምላለሁ! ከእኔ

19፥2 ዘፍ49፥9፤ ዘኍ23፥24
19፥4 2ነገ23፥33-34፤2ዜና36፥4፤ ኢዮ41፥2፤ሰቆ4፥20
19፥5 ዘፍ49፥9፤ 2ነገ23፥34
19፥6 2ነገ24፥9፤ 2ዜና36፥9
19፥7 ሕዝ29፥10፤ 30፥12
19፥8 2ነገ24፥2፡ 11፤ሰቆ4፥20፤ ሕዝ12፥13
19፥9 2ነገ19፥28፤ 24፥15፤25፥7፤ 2ዜና36፥6፤ዘካ11፥3
19፥10 ዘፍ49፥22፤ መዝ80፥8-11፤ ኤር17፥8
19፥11 ሕዝ31፥3፤ ዳን4፥11
19፥12 ዘፍ41፥6፤ ዘዳ29፥28፤ ኢሳ27፥11፤ ሕዝ17፥24፤ 28፥17፤ሆሴ13፥15
19፥13 ሕዝ20፥35፤ ሆሴ2፥3፡14
19፥14 ቍ1፤ ሕዝ 15፥4፤20፥47
20፥1 ዘፍ25፥22፤ ሕዝ1፥1-2፤8፥1፤ 21፥1
20፥3 ዘፍ25፥22፤ 1ሳሙ28፥6፤ ኢሳ1፥15፤ ሕዝ7፥26፤14፥3፤ አሞ8፥12፤ሚክ3፥7

[ሰ]7 ከታርጕም (ሰብዐ ሊቃናት ይመ) ጋር ተመሳሳይ ሲሆን፣ ዕብራይስጡ ግን *ምሽጎቻቸውን ያውቃል* ይላል
[ሐ]10 ከሁለት የጥንት የዕብራይስጥ ቅጆች ጋር ተመሳሳይ ሲሆን አብዛኞዎቹ የጥንት ቅጆች ግን *ያንተ ደም* ይላሉ
[መ]14 ወይም *ከዋና ቅርንጫፎቿ ሥር*

የሚቀርብ በግጥም የተጻፈ እንጕርጕሮ ነው፤ ይሁን እንጂ፣ በብሉይ ኪዳን አብዛኛውን ጊዜ በነቢያት የሚነገረው ሙሾ አንዲት አገር የሚገጥማትን መፈራረስ በምፀት የሚያመለክት ነው (ኢሳ 14፥4-21፤ አሞ5፥1-3 ይመ)፤ እንዲሁም 2፥10 ይመ።

19፥2 *እንዴት ያለች አንበሳ፤* ይህ ምዕራፍ ሙሾ ቢሆንም፣ እንደ ምዕ17 ሁሉ ተራዛሚ ተለዋጭ ዘይቤ ነው። የምዕ17 አምሳያ እዚያው ምዕራፍ ውስጥ የተሰጠ ቢሆንም፣ ለዚህኛው ግን፣ አምሳያው አልተሰጠም። "እንዴት ያለች አንበሳ" ተብላ የተጠቀሰችው ለእስራኤል (ቍ1)፣ ለይሁዳ (4፥6፤ 8፥1፡17፤ 9፥9)፣ ወይም ለኢየሩሳሌም ነው (5፥5)፤ ምክንያቱም ሁሉም ለነገሥታት እናት ናቸውና (ቍ10-14 ይመ)።

19፥3 *ከግልገሎችዋ መካከል አንዱን፤* ለሦስት ወር ብቻ የነገሠውን ዮአኪንን ማለት ነው (2ነገ23፥31-34፤ ኤር22፥10-12 ይመ)። *ሰዎችንም በላ፤* ዘመኑ ጭቁና የተመላበት መሆኑን ያመለክታል (ኤር22፥13 ይመ)።

19፥5 *ሌላውን ወስዳ፤* ምናልባት ለሦስት ወር ብቻ የነገሠውን ዮአኪንን የሚያመለክት ይሆናል (2ነገ24፥8)፤ ይሁን እንጂ በቍ7 ላይ በዝርዝር የተጻፈው ሴዴቅያስን የሚያመለክት ይመስላል። እንደሚታወቀው፣ ሁለቱም ተማርከው ወደ ባቢሎን ተወስደው ነበር (ቍ9)። ይህ ቍጥር የሚያመለክተው፣ ዮአኪንን (2ነገ24፥15) ከሆነ፣ የሐዘን ሙሾው በተገቢው ጊዜ ተደርጎአል ማለት ነው፤ ሴዴቅያስን የሚያመለክተው ከሆነ ግን (2ነገ 25፥7)፣ ወደ ፊት ለሚሆነው ነገር ትንቢት መናገሩ ነው።

19፥10 *እናትህ ... የወይን ተክል መሰለች፤* ቀደም ሲል እንደ እንስት አንበሳ የተጠቀሰችው (ቍ2)፣ አሁን ግን በወይን ተክል ተመስላ ቀርባለች (15፥2 እና ማብ ይመ፤ 17፥7 ይመ)።

19፥12 *የምሥራቅ ነፋስ፤* ናቡከነፆርንና የጦር ሰራዊቱን የሚያመለክት ነው (የ17፥10 ማብ ይመ)።

19፥13 *በበረሓ፤* በእስራኤላውያን ዘንድ፣ እንደ ምድረ በዳ የምትቈጠረውን የባቢሎንን ምድር ማለት ነው (20፥35 ይመ)።

19፥14 *ከዋና ቅርንጫፎቿ ከአንዱ፤* ሴዴቅያስን ነው። *እሳት፤* ዐመፅ ማለት ነው (2ነገ 24፥20 ይመ)። *ለሐዘን እንጕርጕሮም ይሆናል፤* በተደጋጋሚ የሚነገር ሙሾ መሆኑን ያመለክታል (መዝ 137፥1 ይመ)።

20፥1 *በሰባተኛው ዓመት፣ በአምስተኛው ወር፣ ከወሩም በዐሥረኛው ቀን፤* ነሐሴ 14/591 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው፤ የእግዚአብሔር ቃል ወደ ሕዝቅኤል ሲመጣ ይህ ሦስተኛው ቀን ነው (1፥2፤ 8፥1 ይመ)። ሕዝቅኤል ከዚህ በፊት ብዙ ራእዮችን ከእግዚአብሔር የተቀበለ ቢሆንም፣ (ከምዕ12-18 ላይ ያሉትን የየምዕራፉን የመጀመሪያ ቍጥር ይመ)፤ እዚህ ላይ ቀኑ ተለይቶ መጠቀሱ፣ የዚህን ምዕራፍ አስፈላጊነት በአጽንዖት ያሳያል። እንደ ምዕ16 እና 23 ሁሉ ይህ ምዕራፍ የእስራኤልን ታሪክ አሉታዊ ገጽታ ያሳያል፤ የአንድምታ ትርጓሜ ይዘት ግን የለውም። *ከእስራኤል ሽማግሌዎች፤* የ8፥1፤ 14፥1 ማብ ይመ። *ሊጠይቁ፤* ቍ3 እና የ14፥3 ማብ ይመ።

ጠይቃችሁ እንድትረዱ አልፈቅድም"፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።'

[4]"የሰው ልጅ ሆይ፤ እነዚህን ለፍርድ ታቀርባቸዋለህን? በውኑ ለፍርድ ታቀርባቸዋለህን? የቀድሞ አባቶቻቸውን አስጸያፊ ተግባር ግለጽላቸው፤ [5]እንዲህም በላቸው፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "እስራኤልን በመረጥሁበት ቀን፣ ለያዕቆብ ቤት ዘር እጄን አንሥቼ ማልሁላቸው፤ በግብፅም ራሴን ገለጥሁላቸው። እጄንም አንሥቼ፣ 'እኔ እግዚአብሔር አምላካችሁ ነኝ' አልኋቸው። [6]በዚያን ቀን፣ ከግብፅ አውጥቻቸው ከምድር ሁሉ ይልቅ ውብ ወደ ሆነችው ማርና ወተት ወደምታፈስሰው፣ ወዳዘጋጀሁላቸውም ምድር እንደማስገባቸው ማልሁላቸው።" [7]እኔም፣ "እያንዳንዳችሁ ዐይኖቻችሁን ያሳረፋችሁባቸውን ርኩስ ምስሎች አስወግዱ፤ በግብፅ ጣዖታትም ራሳችሁን አታርክሱ፤ እኔ እግዚአብሔር አምላካችሁ ነኝ" አልኋቸው።

[8]" 'እነርሱ ግን በእኔ ላይ ዐመፁ፤ ሊሰሙኝም አልፈለጉም፤ ዐይኖቻቸውን ያሳረፉባቸውን ርኩስ ምስሎች አላስወገዱም፤ የግብፅንም ጣዖታት አልተዉም። እኔም በዚያው በግብፅ ምድር መዓቴን በላያቸው ላፈስ፣ ቍጣዬንም ላወርድባቸው ወስኜ ነበር። [9]ነገር ግን በመካከላቸው በኖሩባቸውና እስራኤልን ከግብፅ ምድር ለመታደግ ቃል ስገባ፣ በእነርሱ ዘንድ በተገለጥሁት በአሕዛብ ፊት ስሜ እንዳይረክስ ስለ ስሜ ክብር ተቈጠብሁ። [10]ስለዚህ ከግብፅ አውጥቼ ወደ ምድረ በዳ አመጣኋቸው። [11]ሰው ቢጠብቀው ኖሮ በሕይወት የሚኖርበትን ሥርዐቴን ሰጠኋቸው፤ ሕጌንም አስታወቅኋቸው። [12]ደግሞም እኔ እግዚአብሔር እንደ ቀደስኋቸው ያውቁ ዘንድ፣ በእኔና በእነርሱ መካከልም ምልክት እንዲሆን ሰንበቴን ሰጠኋቸው።

[13]" 'ነገር ግን የእስራኤል ሕዝብ በምድረ በዳ ዐመፀብኝ፤ ሰው ቢጠብቀው በሕይወት የሚኖርበትን ሥርዐቴን አልጠበቁም፤ ሕጌንም ተላለፉ፤ ሰንበቴንም ፈጽሞ አረከሱ። እኔም መዓቴን ላፈስባቸው፣ በምድረ በዳም ላጠፋቸው ወስኜ ነበር። [14]ነገር ግን ከመካከላቸው ሳወጣቸው በዩ አሕዛብ ፊት ስሜ እንዳይረክስ ስለ ስሜ ተቈጠብሁ። [15]ደግሞም ከምድር ሁሉ ይልቅ ውብ ወደ ሆነችው፣ ማርና ወተት ወደምታፈስሰው፣ ወደ ሰጠኋቸውም ምድር እንደማላስገባቸው እጄን አንሥቼ በምድረ በዳ በፊታቸው ማልሁ፤ [16]ምክንያቱም ሕጎቼን ተላልፈዋል፤ ሥርዐቴን አልጠበቁም፤ ሰንበቴንም አርክሰዋል፤ ልባቸው ከጣዖቶቻቸው ጋር ተጣብቆ አልና። [17]እኔ ግን በርኅራኄ ተመለከትኋቸው እንጂ አላጠፋኋቸውም፤ በምድረ በዳም አልፈጀኋቸውም። [18]ለልጆቻቸው በምድረ በዳ እንዲህ አልኋቸው፤ "የአባቶቻችሁን ሥርዐት አትከተሉ፤ ወጋቸውን አትጠብቁ፤ ራሳችሁንም በጣዖቶቻቸው አታርክሱ። [19]እኔ እግዚአብሔር አምላካችሁ ነኝ፤ ሥርዐቴን ተከተሉ፤ ሕጌንም ለመጠበቅ ትጉ። [20]በእኔና በእናንተ መካከል ምልክት ይሆን ዘንድ ሰንበቴን የተቀደሰ ቀን አድርጉት፤ እኔ እግዚአብሔር አምላካችሁ እንደ ሆንሁም ታውቃላችሁ።"

[21]" 'ልጆቻቸው ግን በእኔ ላይ ዐመፁ፤ ሰው ቢጠብቀው በሕይወት የሚኖርበትን ሥርዐቴን አልተከተሉም፤ ሕጌን ለመጠበቅ አልተጉም፤ ሰንበቴንም አረከሱ። እኔም በምድረ በዳ መዓቴን አፈስባቸዋለሁ፤ ቍጣዬንም

20፥4 ሕዝ16፥2፤ 22፥2፤ማቴ23፥32
20፥5 ዘፍ14፥22፤ ዘሌ11፥44፤ ዘኍ14፥30፤ዘዳ7፥6
20፥6 ዘፀ3፥8፤6፥8፤ ዘዳ8፥7፤ዳን8፥9፤ 11፥41፤ሚል3፥12
20፥7 ዘፀ20፥2፡4፤ ዘሌ18፥3፤ዘዳ29፥18፤ ሕዝ6፥9
20፥8 ዘፀ32፥7፤ ዘዳ 9፥7፤ ኢሳ63፥10፤ኤር7፥26፤ 11፥10፤ሕዝ7፥8፤ 16፥26
20፥9 ኢሳ48፥11፤ ሕዝ36፥22፤39፥7
20፥10 ዘፀ13፥18፤ 19፥1
20፥11 ዘፀ20፥1-23፤ ዘሌ18፥5፤ ዘዳ4፥7-8፤ሕዝ18፥9፤ ሮሜ10፥5
20፥12 ዘፀ20፥10፤ 31፥13፤ዘሌ20፥8፤ ኤር17፥22
20፥13 ቍ24፤ ዘፀ32፥10፤ዘሌ26፥15፡ 43፤ዘኍ14፥29፤ ዘዳ9፥8፤መዝ78፥40፤ 95፥8-10፤ኢሳ56፥6፤ ኤር6፥19፤11፥8
20፥14 ኢሳ48፥11፤ ሕዝ36፥23
20፥15 ዘኍ14፥22 -23፤ዘዳ1፥34፤ መዝ95፥11፤106፥26፤ ዕን3፥11
20፥16 ቍ24፤ ዘኍ15፥39፤ ኤር11፥8፤ሕዝ6፥4፤ አሞ2፥4፤5፥26
20፥17 ኤር4፥27
20፥18 2ዜና30፥7፤ መዝ106፥39፤ ዘካ 1፥4
20፥19 ዘፀ20፥2፤ ዘዳ5፥32-33፤6፥1-2፤ 8፥1፤11፥1፤12፥1
20፥20 ዘፀ20፥10፤ 31፥13፤ኤር17፥22
20፥21 ዘኍ25፥3፤ ኤር7፥26፤ሕዝ7፥8

20፥3 *በሕይወቴ እምላለሁ፤* የ18፥3 ማብ ይመ:: *ልትጠይቁ መጣችሁን፤* የ14፥3 ማብ ይመ::

20፥5 *በመረጥሁበት፣* "መምረጥ" የሚለው ቃል በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ እዚህ ብቻ ይገኛል:: ከቍ5-26 ባለው ክፍል የእስራኤል ታሪክ በሦስት ክፍል ቀርቦአል፤ የመጀመሪያው ክፍል ከቍ 5-9 ግብፅ፣ ከቍ10-17 ምድረ በዳ ነው፤ ሁለተኛው ክፍል ከቍ18-26 ምድረ በዳ ነው፤ ሆኖም የቍ28 ማብ ይመ:: እያንዳንዱ ክፍል አራት ትዕይንቶች አሉት፤ እነርሱም 1)ራእይ 2)ዐመፅ 3)ቍጣ 4)እንደ ገና መጐብኘት ናቸው:: *እጄን አንሥቼ፤* ቃለ መሐላ በሚደረግበት ጊዜ ሁለት እጆችን ወደ ላይ ማንሣት የተለመደ ድርጊት ነበር (ቍ15፡ 23፡ 42 ይመ):: *እኔ እግዚአብሔር አምላካችሁ ነኝ፤* ዘፀ3፥6፡14-15 እና ማብ ይመ::

20፥6 *ማርና ወተት ወደምታፈስሰው ... ምድር፤* የዘፀ 3፥8 ማብ ይመ:: *ከምድር ሁሉ ይልቅ ውብ ወደሆነችው ... ምድር፤* የምድሪቱን የተፈጥሮ ውበት ከዘዳ8፥7-10፤ ኤር3፥19 ጋር ያነጻጽሩ:: እውነተኛው ውበትዋ ደግሞ፣ የእግዚአብሔር የማደሪያው ስፍራ ሆና መመረጥዋ ነው (ዘዳ12፥5፡11 ይመ)::

20፥7 *ጣዖታት፤* የ6፥4 ማብ ይመ::

20፥8 *ዐመፁ፤* ቍ13፡ 21፤ ኢሱ24፥14 ይመ:: *እኔም ... መዓቴን በላያቸው ላፈስ ... ነበር፤* ኪዳኑን በማሰብ መቈጠቡን ያመለክታል (ቍ13፡ 21 ይመ)፤ የ7፥8 ማብ ይመ:: *ቍጣዬን ላወርድባቸው፤* የ5፥13 ማብ ይመ::

20፥9 *እንዳይረክስ፤* መሰደቢያና መሣለቂያ እንዳይሆን ማለት ነው (ዘኍ14፥15-16 ይመ):: *ስለ ስሜ፤* ቍ14፡22፡44 ይመ:: በመጽሐፍ ቅዱስ፣ ስምና ባለቤቱ እጅግ የተያያዙ ናቸው:: ለእግዚአብሔር፣ ስሙ የእርሱነቱ መታወቂያውና የባሕርዩ መገለጫ ነው፤ በዚህም ዝናው ይታወቃል:: ይህ ሐረግ፣ "ስለ ራሴ ስል" ከሚለው ጋር አንድ ነው (ከኢሳ37፥35፤ 43፥25 ጋር ያነጻጽሩ):: ባለፈውም ዘመን ሆነ በሚመጣው ዘመን የእግዚአብሔር የማዳን ኀይሉ እውነተኛ ባሕርዩን የሚገልጽ ሲሆን፣ መታወቂያ ምልክቱም ነው (36፥22፤ መዝ23፥3፤ ኢሳ48፥9 ይመ)::

20፥10 *ምድረ በዳ፤* ይህ ሁለተኛው ክፍል ነው (የቍ5 ማብ ይመ)::

20፥11 *በሕይወት የሚኖርበትን፤* ቍ13፡ 21 ይመ፤ ከቍ25 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ16፥6፤ 18፥9 ማብ ይመ፤ ዘሌ18፥5 እና ማብ ይመ::

20፥12 *ምልክት እንዲሆን ሰንበቴን፤* እስራኤል ሰንበትን ማክበርዋ፣ የእግዚአብሔር ቅዱስ ሕዝብ መሆንዋ እንዲታወቅ የተሰጠ ምልክት ነው (ዘፀ31፥13-17 ይመ):: እንደ ኤርምያስ ሁሉ (ኤር17፥19-27፤ ከነህ13፥17-18 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ሕዝቅኤልም (22፥8፡26፤ 23፥38፤ 44፥24፤ 45፥17፤ 46፥3 ይመ) ለሰንበት በከፍተኛ ትኩረት ሰጥቶአል:: በኋለኛው ዘመን ግን፣ የአይሁድ እምነት ወግ አጥባቂዎች የሰንበትን ሕግ አዛብተዋል (ማቴ12፥1-14 ይመ)::

20፥13 *አረከሱ፤* የሰንበትን ዕረፍት ባለመጠበቅ ሳይሆን (ኤር17፥21-23)፣ እግዚአብሔር በሚፈልግበት መንገድና መንፈስ ባለማክበራቸው ነበር (አሞ8፥5)::

20፥18 *ለልጆቻቸው ... እንዲህ አልኋቸው፤* ይህ ሦስተኛው ክፍል ነው (የቍ5 ማብ ይመ)፤ እግዚአብሔር በምድረ በዳ ይህን ሐሳብ ለልጆቻቸው በአዲስ መልክ ተናገረ (ዘኍ14፥26-35 ይመ)::

አወርድባቸዋለሁ ብዬ ነበር:: 22ነገር ግን
ከግብፅ ሳወጣቸው ባዩ አሕዛብ ፊት ስሜ
እንዳይረክስ እጄን ሰበሰብሁ:: 23ደግሞም
በአሕዛብ መካከል እንደምበትናቸውና ወደ
ተለያዩ አገሮች እንደማፈልሳቸው በምድረ
በዳ እጄን አንሥቼ በፊታቸው ማልሁ፤
24ምክንያቱም ሥርዐቴን አቃለሉ፤ ሰንበቴን
አረከሱ እንጂ ሕጌን አልጠበቁም፤ ዐይናቸ
ውም ከአባቶቻቸው ጣዖታት ጋር ተጣብቆ
አል:: 25እኔም መልካም ላልሆነ ሥርዐትና
በሕይወት ለማይኖሩበት ሕግ አሳልፌ ሰጠ
ኋቸው፤ 26እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ
እንዲያውቁ፣ አስደነግጣቸውም ዘንድ በእሳት
በሚያቀርቡት የበኵር ልጅ *መሥዋዕት* እን
ዲረክሱ አደረግኋቸው::'ሙ

27"ስለዚህ የሰው ልጅ ሆይ፤ ለእስራኤል
ሕዝብ እንዲህ ብለህ ተናገር፤ 'ጌታ *እግዚ
አብሔር* እንዲህ ይላል፤ "አባቶቻችሁ እኔን
በመተው በዚህ ደግሞ አቃለሉኝ፤ 28ልስጣ
ቸው ወደ ማልሁላቸው ምድር ባስገባኋቸው
ጊዜ፣ ከፍ ያለውን ኰረብታ ሁሉና የለመለ
መውን ዛፍ ሁሉ ተመለከቱ፤ በዚያም
*መሥዋዕታቸውን* ሠዉ፤ ቍርባናቸውን በማ
ቅረብ ቍጣዬን አነሣሡ፤ መልካም መዐዛ
ያለውን ዕጣናቸውን ዐጠኑ፤ የመጠጥ ቍር
ባናቸውንም አፈሰሱ::" 29እኔም፣ "የምትሄ
ዱበት ይህ ከፍታ ቦታ ምንድን ነው?"
አልኋቸው::' እስከ ዛሬም ድረስ ስሙ ባማሩ
ተብሎ ይጠራል::

## ቅጣትና ምሕረት

30"ስለዚህ ለእስራኤል ቤት እንዲህ በል፤
'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "አባ
ቶቻችሁ እንዳደረጉት ራሳችሁን ታረክሳላ
ችሁን? በረከሱ ምስሎቻቸው ምኞት
ትቃጠላላችሁን? 31ቍርባናችሁን በምታቀር
ቡበት ጊዜ ልጆቻችሁን ለእሳት በመዳረግሰ
እስከ ዛሬ ድረስ በጣዖቶቻችሁ ሁሉ እየረ
ከሳችሁ ናችሁ:: የእስራኤል ቤት ሆይ፤
ታዲያ የእኔን ሐሳብ እንድትጠይቁ ልፈቀ
ድላችሁን? በሕያውነቴ እምላለሁ! እንድትጠ
ይቁኝ አልፈቅድም፤ ይላል ጌታ *እግዚአ
ብሔር*::"

32" 'እናንተም፣ "ለዕንጨትና ለድንጋይ እን
ደሚሰግዱ እንደ አሕዛብ፣ በዓለምም እንደ
ሚኖረው ሕዝብ ሁሉ እንሁን" አላችሁ፤
ነገር ግን በልባችሁ ያሰባችሁት ከቶ አይሆ
ንላችሁም:: 33በሕያውነቴ እምላለሁ ይላል
ጌታ *እግዚአብሔር*፤ በብርቱ ክንድና በተዘ
ረጋች እጅ፣ *መዓትንም* በማፍሰስ በላያችሁ
እነግሣለሁ:: 34ከአሕዛብ መካከል አወጣች
ኋለሁ፤ በብርቱ ክንድና በተዘረጋች እጅ
*መዓትንም* በማፍሰስ ከተበተናችሁባቸውም
አገሮች ሁሉ እሰበስባችኋለሁ:: 35ወደ አሕ
ዛብ ምድረ በዳ አመጣችኋለሁ፤ በዚያም
ፊት ለፊት ከእናንተ ጋር እፋረዳለሁ::
36በግብፅ ምድረ በዳ ከአባቶቻችሁ ጋር
እንደ ተፋረድሁ፣ ከእናንተም ጋር እፋረ
ዳለሁ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*:: 37ከበትሬ
በታች አሳልፋችኋለሁ፤ ከቃል ኪዳኔም
ጋር አጣብቃችኋለሁ:: 38በእኔ ላይ ያመፁ
ትንና የበደሉኝን ከመካከላችሁ አስወግዳለሁ፤
ከሚኖሩበት አገር አወጣቸዋለሁ፤ ወደ እስ
ራኤል ምድር ግን አይገቡም፤ በዚያን ጊዜ
እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃ
ላችሁ::

39" 'የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ስለ እናንተ
ግን ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "የማ
ትሰሙኝ ከሆነ፣ እያንዳንዳችሁ ሂዱና
ለጣዖታቶቻችሁ ስገዱ! ነገር ግን በቍርባና
ችሁና በጣዖቶቻችሁ ቅዱሱን ስሜን ከእንግ
ዲህ አታረክሱም:: 40በቅዱሱ ተራራዬ፣ ከፍ
ባለው የእስራኤል ተራራ ላይ በዚያ ምድር
የእስራኤል ቤት ሁሉ ያመልከኛልና ይላል
ጌታ *እግዚአብሔር*፤ እኔም በዚያ እቀበ
ላቸዋለሁ:: ቍርባናችሁንና በኵራታችሁን
ከተቀደሱ *መሥዋዕቶቻችሁ* ሁሉ ጋር በዚያ

20፥22 መዝ78፥38፤ ኢሳ48፥11
20፥23 ዘሌ26፥33፤ መዝ9፥11
20፥24 ቍ13፡16፤ ሕዝ2፥3፤6፥9፤18፥6፤ አሞ2፥4
20፥25 መዝ81፥12፤ ኢሳ66፥4፤ሮሜ1፥28፤ 2ተሰ2፥11
20፥26 ዘሌ18፥21፤ 20፥2-5፤2ነገ17፥17
20፥27 ዘኍ15፥30፤ መዝ78፥57፤ ሕዝ 18፥24፤ ሮሜ2፥24
20፥28 ነህ9፥23፤ መዝ78፥55፡58፤ ኤር2፥7፤3፥6፤ 19፥13፤ሕዝ6፥13
20፥29 ሕዝ16፥16፤ 43፥7
20፥30 ቍ43፤ መሳ2፥16-19፤ ኤር16፥12
20፥31 መዝ106፥37-39፤ ኤር7፥31፤ ሕዝ14፥3፤16፥20፤ አሞ8፥12፤ዘካ7፥13
20፥33 ኤር21፥5፤ ሕዝ16፥27፤25፥16
20፥34 ዘዳ30፥4፤ መዝ106፥47፤ ኢሳ 27፥12-13፤ 31፥3፤ኤር44፥6፤ ሰቆ2፥4፤ሕዝ6፥14፤ 2ቆሮ6፥17
20፥35 1ሳሙ12፥7፤ ኢዮ22፥4፤ኤር2፥35፤ ሕዝ19፥13
20፥36 ዘኍ11፥1 -35፤14፥28-30፤ 1ቆሮ10፥5-10
20፥37 ዘሌ27፥32፤ ሕዝ16፥62
20፥38 መዝ95፥11፤ ኤር44፥14፤ ሕዝ13፥9፤23፥49፤ 34፥17-22፤ሆሴ2፥14፤ አሞ9፥9-10፤ ዘካ13፥8-9፤ ሚል3፥3፤4፥1-3፤ ዕብ4፥3
20፥39 ዘፀ20፥7፤ ኤር44፥25፤ሕዝ13፥19፤ ሕዝ43፥7፤አሞ4፥4
20፥40 ኢሳ56፥7፤ 60፥7፤ሕዝ17፥22፤ 34፥14፤ሚል3፥4

ሙ26 *ወይም የበኵር ልጅን ሁሉ በእሳት ውስጥ በማሳለፍ*
ሩ29 *ባማ ማለት ከፍታ ቦታ ማለት ነው*
ሰ31 *ወይም ልጆቻችሁን በእሳት ውስጥ በማሳለፍ*

*20፥25-26፤* በሮሜ1፥24-32 ከተገለጸው መለኮታዊ መርሕ
ጋር ይህን ያነጻጽሩ::

20፥26 *እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ እንዲያውቁ፤*
ልጆቻቸው እስኪያውቁት የትም ድረስ ቢሆን ይሄዳል (የ5፥13
ማብ ይመ):: *በሚያቀርቡት የበኵር ልጅ መሥዋዕት፤* ቍ31
ይመ፣ እንዲሁም የ16፥20 ማብ ይመ::

20፥28 *ወደ ... ምድር ባስገባኋቸው ጊዜ፤* በሕዝቅኤል
ታሪክ ውስጥ አራተኛው ክፍል ነው (የቍ5 ማብ ይመ)፤ ይሁን
እንጂ ይህ ክፍል እንደሌሎቹ ሂደቱን እስከ መጨረሻው ድረስ
አሟልቶ የያዘ አልነበረም::

20፥30 *ታረክሳላችሁን?* የምዕራፉ መሪ ሐሳብ ነው::

20፥31 *እንድትጠይቁ፤* የ14፥3 ማብ ይመ::

20፥32 *እንደ አሕዛብ፤* እስራኤላውያን የራሳቸውን ማንነት
ትተው በዙሪያቸው እንዳሉት እንደ ሌሎች ሕዝቦች ለመሆን ብዙ
ጊዜ ጥረዋል (1ሳሙ8፥5 ይመ):: *ከቶ አይሆንላችሁም፤* ወደ ግብፅ
ተማርከው የሄዱት እንደደረሰባቸው ማለት ነው (ኤር 44፥15-19)::

20፥33 *በብርቱ ክንድና በተዘረጋች እጅ፤* አባባሉ የእስራ
ኤል ሕዝብ ከምድረ ግብፅ በወጣ ጊዜ የተነገረለት ነው (ከዘዳ
4፥34፤ 5፥15፤ 7፥19፤ 11፥2፤ 26፥8 ጋር ያነጻጽሩ)::

20፥35 *ወደ አሕዛብ ምድረ በዳ፤* ለእስራኤላውያን ተማር
ከው አሕዛብ መሄድ ማለት ወደ ተስፋዪቱ ምድር ሲሄዱ የተጓ
ዙትን የምድረ በዳ ሕይወት ማለት ነው (ሆሴ2፥14)::

20፥37 *ከበትሬ በታች አሳልፋችኋለሁ፤* የበጎች እረኛ
በጎቹን በበትሩ እንደሚቈጥራቸው ወይም የራሱ በጎች ከሌሎች
እንደሚለያቸው ማለት ነው (ኤር33፥13፤ ማቴ25፥32-33)::

20፥38 *አስወግዳለሁ፤* እንደ መጀመሪያው የምድረ በዳ
ጕዞው ሁሉ እንደ ነበራቸው ሁኔታ፣ አብዛኞቹ ወደ ተስፋዪቱ
ምድር እንዲገቡ አልተፈቀደላቸውም ነበር (ዘኍ14፥26-35 ይመ)::

20፥39 *ሂዱና ለጣዖታቶቻችሁ ስገዱ፤* አባባሉ የምፀት
አነጋገር ነው (ከ1ነገ22፥15፤ አሞ4፥4 ጋር ያነጻጽሩ)::

20፥40 *በቅዱሱ ተራራዬ፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ
የተጠቀሰው እዚህ ላይ ብቻ ነው፤ የሚያመለክተውም ጽዮንን ወይም
ኢየሩሳሌምን ነው (መዝ2፥6፤ 3፥4፤ 15፥1 ይመ)፤ እንዲሁም
ኢሳ11፥9፤ 56፥7፤ 57፥13፤ 65፥11፤ አብ16፤ ሶፎ3፥11 ይመ)::
*የእስራኤል ቤት ሁሉ፤* ይህ ሐረግ ከ722-721 ዓ.ቅ.ክ. በአሦር
የተያዘውን የሰሜኑንም መንግሥት ይመለከታል (11፥15፤ 36፥10
ይመ):: *መሥዋዕቶቻችሁ፤* ምናልባት ሕጉ የሚያዝዘውን *መሥዋዕት*
ሊሆን ይችላል፤ በዚሁ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ከም44-48

እሻለሁ:: [41]ከሕዝቦች መካከል ባወጣኋችሁ ጊዜ፣ ከተበተናችሁባቸውም አገሮች በሰበሰብኋችሁ ጊዜ፣ መልካም መዐዛ እንዳለው ዕጣን እቀበላችኋለሁ፤ በእናንተም መካከል ቅዱስ መሆኔን በአሕዛብ ፊት እገልጣለሁ:: [42]ለአባቶቻችሁ ልሰጥ እጄን አንሥቼ ወደማልሁላቸው ምድር ወደ እስራኤል አገር በማስገባችሁ ጊዜ፣ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ:: [43]በዚያም መንገዳችሁንና ራሳችሁን ያረከሳችሁበትን ተግባር ሁሉ ታስታውሳላችሁ፤ በፈጸማችሁትም ክፋት ሁሉ ራሳችሁን ትጸየፋላችሁ:: [44]የእስራኤል ቤት ሆይ፤ እንደ ክፉ መንገዳችሁና እንደ ብልሹ ተግባራችሁ ሳይሆን፣ ስለ ስሜ ስል በምጐበኛችሁ ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::' "

## በደቡብ አገር ላይ የተነገረ ትንቢት

[45]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [46]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ ደቡብ አዙር፤ በደቡብ ላይ ቃል ተናገር፤ በደቡብ አገር ደን ላይም ትንቢት ተንብይ:: [47]ለደቡቡ ደን እንዲህ በል፤ '*የእግዚአብሔርን* ቃል ስማ፤ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "በአንተ ላይ እሳት ልለኵስ ነው፤ እሳቱ የለመለመውንና የደረቀውን ዛፍህን ሁሉ ይበላል፤ የሚንቦገቦገው ነበልባሉም አይጠፋም፤ ከደቡብ እስከ ሰሜን ያለውን ፊት ሁሉ ይለበልባል:: [48]ሰው ሁሉ እኔ *እግዚአብሔር* እንዳነደድሁት ያያል፤ የሚያጠፋውም የለም::' "

[49]እኔም፤ "ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ወዮ! እነርሱ ስለ እኔ፣ 'ተምሳሌት ብቻ ይመስላል' ይሉኛል" አልሁ::

20+41 ዘጸ30+4፤ ኢሳ5+16፤ሕዝ11+7፤ 28+25፤36+23፤ 2ቆሮ2+14፤6+17
20+42 ኤር23+8፤ 30+3፤ሕዝ34+13:27፤ 36+24፤37+21፤ 38+23
20+43 ዘሌ26+41፤ ሕዝ6+9፤14+22፤ 16+61፤ሆሴ5+15
20+44 መዝ109+21 ፤ኢሳ43+25፤ሕዝ 16+62፤36+22:32
20+46 ኢሳ30+6፤ ኤር13+19፤ሕዝ4+3፤ 13+17፤21+2፤ አሞ7+16
20+47 2ነገ19+23፤ ኢሳ9+18-19፤13+8፤ ሕዝ19+14፤21+4
20+48 ኤር7+20፤ ሕዝ21+5:32፤23+25
20+49 መሳ14+12፤ መዝ78+2፤ ሕዝ4+14፤12+9፤ ማቴ13+13፤ዮሐ16+25
21+1 ሕዝ20+1
21+2 ኤር26+11 -12፤ሕዝ9+6፤13+7፤ 20+46
21+3 ቍ9-11፤ ኢዮ9+22፤ኢሳ27+1፤ 57+1፤ኤር21+13፤ 47+6-7፤ሕዝ14+21
21+4 ዘሌ26+25፤ ኤር25+27፤ ሕዝ20+47
21+5 ቍ30፤ ኢሳ34+5፤ ሕዝ20+47-48፤ ናሆ1+9
21+6 ቍ12፤ ኢሳ22+4፤ኤር30+6፤ ሕዝ9+4
21+7 ዘሌ26+36፤ ኢሱ7+5፤ኢዮ11+16፤ 23+2፤መዝ6+2፤ኤር47+3፤ሕዝ22+14
21+10 ዘዳ32+41፤ መዝ110+5-6፤ ኢሳ34+5-6

## የቅጣት በትር የሆነችው ባቢሎን

**21** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ ኢየሩሳሌም አዙር፤ በመቅደሱ ላይ ቃል ተናገር፤ በእስራኤል ምድር ላይ ትንቢት ተንብይ፤ [3]እንዲህም በል፤ '*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ እኔ በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤ ሰይፌን ከሰገባው እመዛለሁ፤ ጻድቁንም፣ ክፉውንም ከአንተ ዘንድ አስወግዳለሁ:: [4]ጻድቁንም ክፉውንም ስለማስወግድ ሰይፌ ከደቡብ ጀምሮ እስከ ሰሜን ባለው ሕዝብ ሁሉ ላይ ከሰገባው ይመዘዛል:: [5]ሰይፌን ከሰገባው የመዘዝሁት እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ሕዝቡ ሁሉ ያውቃል፤ እርሱም ወደ ሰገባው አይመለስም::'

[6]"ስለዚህ የሰው ልጅ ሆይ፤ አቃስት፤ በተሰበረ ልብና በመረረ ሐዘን አቃስት፤ [7]እነርሱም፣ 'ለምን ታቃስታለህ?' ቢሉህ፣ "ስለሚመጣው ክፉ ወሬ ነው፤ ልብ ሁሉ ይቀልጣል፤ እጅም ሁሉ ይዝላል፤ ነፍስ ሁሉ ይደክማል፤ ጕልበትም ሁሉ ውሃ ይሆናል' በላቸው:: እነሆ ይመጣል፤ ይፈጸማልም፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::"

[8]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [9]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በል፤ '*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

"ሰይፍ! ሰይፍ!
የተሳለ የተወለወለም፤
[10]የተሳለው ሊገድል፣
የተወለወለውም እንደ መብረቅ

ሌሎቹ 19 "መሥዋዕት" የሚሉ ቃላት በዕብራይስጡ ተጠቅሰዋል፤ የሚያመለክተውም ለቤተ መቅደሱ ወይም ለካህናት ተለይቶ የተመደበውን መሬት (45+1፤ 48+8-10 ይመ) ወይም ለካህናቱ ልዩ ስጦታ እንዲሆን የተመደበ ውን መሬት የሚያመለክት ነው (44+30 ይመ):: *ቍርባናችሁን፤* በፈቃደኝነት የሚዋጣውን መዋጮ ነው:: *እሻለሁ፤* በዘዳ23+21፤ ሚል 6+8 ይመ::

20+41 *ባወጣኋችሁ፤* ከቍ34 ጋር ያነጻጽሩ:: *መልካም መዐዛ እንዳለው ዕጣን፤* ይህ ቃል በቃል (6+13) ወይም በተለዋጭ ዘይቤ የቀረበ ይሆናል (ኤፌ5+2)::

20+43 *መንገዳችሁን ... ታስታውሳላችሁ ... ራሳችሁን ትጸየፋላችሁ፤* ፍጹም በሆነ መንገድ ንስሓ ይገባሉ ማለት ነው (6+9፤ 16+63፤ 36+31፤ ሉቃ15+17-19 ይመ)::

20+44 *ስለ ስሜ ስል፤* የሕዝቅኤልን ንግግር ጠቅለል ባለ መልኩ፤ የሚያመለክት መደምደሚያ ነው (የቍ9 ማብ ይመ)::

20+46 *ፊትህን ... አዙር፤* ሕዝቅኤል በዚህ ሁኔታ ከእንዲታይ ስምንት ጊዜ ተነግሮታል (13+17፤ 21+2፤ 25+2፤ 28+21፤ 29+2፤ 35+2፤ 38+2):: *ወደ ደቡብ፤* ወደ ይሁዳና ወደ ኢየሩሳሌም ማለት ነው፤ ይህም ሕዝቅኤል በእነዚህ ምዕራፎች የተናገራቸው ትንቢቶች ሁሉ የሚመለከቱት እነዚህን አገሮች በመሆኑ ነው፤ ወደዚች ምድር ያነጣጠረ ማንኛውም የባቢሎን ወራሪ ኀይል፣ ምን ጊዜም የሚወጣው ከሰሜን ወደ ደቡብ ነው (26+7 ይመ)::

20+47 *እሳት ... ልለኵስ ነው፤* የወራሪ ኀይሎችን የሚገልጽ ዘይቤያዊ አባባል ነው (ኢሳ10+16-19፤ ኤር15+14፤ 17+4: 27፤ 21+14፤ 15+7 ማብ ይመ):: *የለመለመውንና የደረቀውን፤* ዛፎችን ሁሉ ማለት ነው (ከ17+24፤ ሉቃ23+31 ያነጻጽሩ):: *ከደቡብ እስከ ሰሜን፤* አቅጣጫን ለማመልከት ሳይሆን፣ እሳቱ ከዳር እስከ ዳር ያለውን ስፍራ ሁሉ እንደሚያዳርስ ለማመልከት ነው::

20+49 *ተምሳሌት፤* የ17+2 ማብ ይመ:: በሌላ ስፍራ ነቢዩን ስለንዳጠጠበት ሁኔታ 12+21-28፤ 33+32 ይመ)::

21+2 *ፊትህን ... አዙር፤* የ20+46 ማብ ይመ:: *መቅደሱንም በመቃወም፤* የ9+6 ማብ ይመ::

21+3 *በአንቺ ላይ፤* የ5+8 ማብ ይመ፤ *ሰይፌ፤* ስለ እግዚአብሔር ፍርድ ሰይፍ ኢሳ31+8፤ 34+6፤ 66+16 ይመ:: አምስቱን የሰይፍ ንግሮች በተመለከተ ነቢዩ ካየው ራእይ ይህ የመጀመሪያው ነው (ቍ8-17: 18-24: 25-27: 28-32) በዚህ ስፍራ ሰይፉ የሚያመለክተው፣ ባቢሎንንና ናቡከደነፆርን ነው (ቍ19):: *ጻደቁንም ክፉውንም፤* በእስራኤል ላይ የሚመጣውን ፍርድ፣ ፍጹምነት ያመለክታል:: ጻድቃንም እንኳ ቢኖሩ፣ ማንም እንደማያመልጥ ያሳያል:: እግዚአብሔር ኖኅንና (ዘፍ6+7-8) ሎጥን (ዘፍ18+23፤ 19+12-13) እንዴት እንዳዳናቸው ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ::

*21+4፤* የ20+47 ማብ ይመ::

21+6 *በተሰበረ ልብና በመረረ ሐዘን አቃስት፤* ሕዝቅኤል በዚህ ስፍራ የሚገልጠው የሐዘን ልቅሶ ሌላ የትንቢት ምልክትና የማይቀረውንም ፍርድ መልእክት የሚመለከት ነው::

21+7 *ቢሉህ፤* በ12+9 ላይ የተገለጸውን የሕዝቡን ምላሽና የሕዝቅኤልን ሁኔታ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ:: ይህም ሕዝቅኤል ለሰባተኛ ጊዜ ያሳየው ምሳሌያዊ ድርጊት ነው::

21+9 *ሰይፍ! ሰይፍ!* በጥፈራ ወይም በምሳሌያዊ ድርጊት የሚገለጽ የሰይፍ ዘፈን ሳይሆን አይቀርም (የቍ3 ማብ ይመ):: እንዲህ ዐይነቱ ዘፈን የሚዘፈነው ተዋጊዎች ብዙውን ጊዜ ወደ ጦር ሜዳ በሚሄዱበት ወቅት ነው (የ2ሳሙ1+18 ማብ ይመ):: ነገሩ ከሀገራችን ቀረርቶና ሽለላ ጋር የሚመሳሰል ሳይሆን አይቀርም::

*21+10፤* በባቢሎናውያን ከይሁዳ በቀር ሌላውን አገር ሁሉ ያሸንፋሉ ብሎ ማሰብ ከንቱ ተስፋን እንደመመገብ መቈጠሩን

ሊብረቀረቅ ነው!

" 'ታዲያ፣ እንዴት ደስ ሊለን ይችላል? ሰይፉ የልጄን በትረ መንግሥት እንደ ማንኛ ውም በትር ንቆአል::

[11]" 'በእጁ እንዲያዝ፣
ሰይፉ ሊወለወል ተሰጥቶአል፤
ገዳዩ በእጁ እንዲጨብጠው፣
ተስሎአል፤ ተወልውሎአል::
[12]የሰው ልጅ ሆይ፤ ይህ በሕዝቤ ላይ፣
በእስራኤልም መሳፍንት ሁሉ ላይ
መጥቶአልና፤
ጩኽት፣ ዋይታም አሰማ::
እነርሱ ከሕዝቤ ጋር በአንድ ላይ፣
ለሰይፍ ተጥለዋል፤
ስለዚህ ደረትህን ምታ::

[13]" 'ፈተና በእርግጥ ይመጣል፤ ሰይፉ የና ቀው በትረ መንግሥት ዘላቂነት ባይኖረ ውስ? ይላል ጌታ እግዚአብሔር::'

[14]"እንግዲህ፣ የሰው ልጅ ሆይ፤ ትንቢት
ተናገር፤
በእጅህም አጨብጭብ፤
ሰይፉ ሁለት ጊዜ፣
ሦስት ጊዜም ይምታ፤
በእጅጉ የሚገድል፣
ለግድያ የሚሆን፣
በየአቅጣጫውም የሚከባቸው ሰይፍ
ነው::
[15]ልብ ሁሉ ይቀልጥ ዘንድ፣
የሚወድቁትም እንዲበዙ፣
በበሮቻቸው ሁሉ፣
የግድያውን ሰይፍ[*] አኑሬአለሁ::
ወዮ! እንዲያብረቀርቅ ተወልውሎአል፤
ለመግደልም ተመዞአል::
[16]ሰይፍ ሆይ፤ በስለትህ አቅጣጫ ሁሉ፣
ወደ ቀኝም፣
ወደ ግራም ቍረጥ::
[17]እኔም በእጄ አጨብጭባለሁ፤
ቍጣዬም ይበርዳል፤
እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ::"

[18]የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [19]"የሰው ልጅ ሆይ፤ የባቢሎን ንጉሥ ሰይፍ የሚመጣባቸውን የሁለት መንገ ዶች ካርታ ንደፍ፤ መንገዶቹም ከአንድ አገር የሚነሡ ናቸው፤ መንገዱ ወደ ከተማው በሚገነጠልበት ቦታ ላይ ምልክት አቁም:: [20]በአሞናውያን ከተማ በረባት ላይ ለሚመ ጣው ሰይፍ አንደኛውን መንገድ ምልክት አድርግ፤ በይሁዳና በተመሸገችው ከተማ በኢየሩሳሌም ላይ ለሚመጣውም ሰይፍ ሁለተ ኛውን መንገድ ምልክት አድርግ:: [21]የባቢ ሎን ንጉሥ በጥንቈላ ምሪት ለማግኘት በመንታ መንገድ ላይ በሁለቱ ጐዳናዎች መጋጠሚያ ላይ ይቆማል፤ ቀስቶቹን በመወ ዝወዝ ዕጣ ይጥላል፤ አማልክቱን ያማክራል፤ ጕበትንም ይመረምራል:: [22]የቅጥር መደርመሻ አምጥቶ እንዲያቆም፣ ለመግደል ትእዛዝ እንዲሰጥ፣ ፉከራ እንዲያሰማ፣ ቅጥር መደ ርመሻውን በከተሞች በር ላይ እንዲያደርግ፣ የዐፈር ድልድል እንዲያበጅና ምሽግ እንዲ ሠራ የኢየሩሳሌም ዕጣ በቀኝ እጁ ወጣ:: [23]ይህም ከእርሱ ጋር ቃል ኪዳን ለገቡት የተሳሳተ ምሪት ይመስላል፤ እርሱ ግን በደ ላቸውን ያሳስባቸዋል፤ ማርኮም ይዞአቸው ይሄዳል::

[24]"ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'እናንተ በምታደርጉት ሁሉ ኀጢአ ታችሁን በመግለጽ፣ በግልጽም በማመፅ በደ ላችሁን ስላሳሰባችሁ፣ እንዲሁም ስላደረጋ ችሁ በምርኮ ትወሰዳላችሁ::

[25]" 'አንት የግፍ ጽዋህ የሞላ፣ የምትቀ ጣበት ቀን የደረሰ፣ ርኩስና ክፉ የእስራኤል መስፍን ሆይ፤ [26]ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ጥምጥምህን አውልቅ፤ ዘውድህን

21፥11 ኤር46፥4
21፥12 ኤር31፥19
21፥14 ቍ17፤ ዘኍ24፥10፤ ሕዝ6፥11፤30፥24
21፥15 2ሳሙ17፥10፤መዝ22፥14
21፥17 ቍ14፤ ሕዝ5፥13፤6፥11፤ 16፥42፤22፥13
21፥19 ኤር31፥21፤ ሕዝ14፥21፤32፥11
21፥20 ዘዳ3፥11
21፥21 ዘኍ22፥7፤ 23፥23፤ምሳ16፥33፤ ዘካ10፥2
21፥22 2ነገ25፥1፤ ኤር4፥16፤32፥24፤ ሕዝ4፥2፤26፥9
21፥23 ዘኍ5፥15፤ ሕዝ17፥19
21፥25 ሕዝ22፥4፤ 35፥5
21፥26 መዝ75፥7፤ ኢሳ28፥5፤40፥4፤ ኤር13፥18፤ ሕዝ17፥24፤ ማቴ23፥12

[*]15 ከሰብዓ ሊቃናት ጋር ተመሳሳይ ሲሆን በዕብራይስጡ ግን የዚህ ቃል ትርጕም አይታወቅም

ያመለክታል:: *በትር፤* የግዛትን፣ የአስተዳደርን ወይም የመንግሥትን ሥልጣን ያመለክታል:: *የልጄን፤* በቍ12 (ዘፍ49፥9 ይመ) ላይ ሕዝቤ ከሚለው ጋር አንድ ዐይነት ነው:: *ሰይፉ፤* ባቢሎንና ናቡከደነፆር ናቸው (ቍ19 ይመ)::

21፥11 *ለገዳዩ፤* ናቡከደነፆርን ነው (ቍ19)::

21፥12 *ጩኸት፣ ዋይታም ... ደረትህን ምታ፤* ስምንተ ኛው ምሳሌያዊ ድርጊት ነው::

21፥13 *ይመጣል፤* በይሁዳ ላይ ይመጣል ማለት ነው:: *ሰይፍ የናቀው በትረ መንግሥት ዘላቂነት ባይኖረውስ?* የ10ለ ማብ ይመ:: በ586 ዓ.ቅ.ክ. ላይ ያበቃለትን የዳዊትን ሥርወ መንግሥት መቋረጥ ያመለክታል (ቍ25-27 ይመ)::

21፥14 *አጨብጭብ፤* 6፥11 እና ማብ ይመ:: *ሰይፉ ሁለት ጊዜ ይምታ፤* ከ2ነገ 13፥18-19 ጋር ያነጻጽሩ::

21፥17 *በእጄ አጨብጭባለሁ፤* በቍ14 ላይ እግዚአብሔር ለሕዝቅኤል እንደ ሰጠው ትእዛዝ እርሱም የሚያደርግ መሆኑን የሚገልጽ ነው::

21፥19 *የባቢሎን ንጉሥ፤* ናቡከደነፆርን ነው:: *ሁለቱም ከአንድ አገር፤* በባቢሎን ወይም ደግሞ ሶርያ ልትሆን ትችላለች፤ ናቡከደነፆር በሰሜናዊ ሶሪያ የምትገኘውን ሪብለን የጦር እዝ መምሪያው ያደረገበት ጊዜ ነበርና (2ነገ25፥6)::

21፥20 *ረባት፤* የአሞን ዋና ከተማ (ኤር49፥2)፤ ባሁኑ ጊዜ የዮርዳኖስ መንግሥት መዲና (ዋና ከተማ) ናት::

21፥21 *ቀስቶቹን በመወዝወዝ ዕጣ ይጥላል፤* ወደፊት ስለሚደረገው ጦርነት ምልክት ለማግኘት (ለማወቅ) ፍላጻ በመ ወርወር የሚደረግ ጥንቈላ ነው፤ እንዲህ ዐይነቱ አሠራር በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በሌላ ስፍራ አይገኝም፤ ፍላጻዎች በሰገባ ውስጥ ተስተካክለው ይቀመጣሉ፤ በእያንዳንዱ እጅ አንዳንድ ፍላጻ ይወጣል፣ በቀኝ እጅ ተመርጦ የወጣው ፍላጻ የጥሩ ዕጣ ምልክት ሆኖ ይቈጠራል (ቍ22 ይመ):: *አማልክቱን፤* የዕብራይ ስጡ ቃል፣ በዘፍ31፥19 ላይ የቤተ ሰው ጣዖት ተብሎ ተተርጕ ሞአል:: ጣዖቶችን ስለ መጠየቅ በሆሴ3፥4፤ በዘካ10፥2 ላይ ተጠ ቅሶአል:: በዘፍ31፥19-35 የተጠቀሰው የቤተ ሰው ጣዖት ትንሽ ቅርጽ ነገር ከመሆኑ የተነሣ በኮርቻ ሥር ሊደበቅ ችሎአል፤ ሌሎቹ ግን በሰው ቍመት ልክ የተሠሩ ናቸው (1ሳሙ19፥13-16):: *ጕበትም ይመረምራል፤* የበግን ጕበት ቀለምና አሠራሩን በመመርመር ስለ ወደ ፊቱ ማወቅ፣ በጥንት ባቢሎን የተለመደ ነበር፤ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በሌላ ስፍራ አልተጠቀሰም::

21፥23 *የተሳሳተ ምሪት፤* ቀድሞ ለናቡከደነፆር ተገዥ ዎች የነበሩትና በዚህ ጊዜ ያመፁት የኢየሩሳሌም መሪዎች (2ነገ24፥20) ምልክት መመርመራቸው (ቍ21-22) እንዲሁም ተስፋ ማድረጋቸው ስሕተት መሆኑን ተገነዘቡ::

21፥25 *የእስራኤል መስፍን፤* ሴዴቅያስን ነው (የ7፥27 ማብ ይመ)::

21፥26 *ጥምጥምህን፤* በነገሥታት ራስ ላይ መሆኑ በዚህ ስፍራ ብቻ ተጠቅሶአል:: በሌላ ስፍራ አክሊል የሚደፋበትን ለማመልከት

ባል፤ እንደ ከዚህ በፊቱ አይሆንም፤ ዝቅ ያለው ከፍ ይላል፤ ከፍ ያለውም ዝቅ ይላል:: [27]ባድማ! ባድማ! ባድማ አደርጋታለሁ፤ የሚገባው ባለ መብት እስከሚመጣ ድረስ እንደ ቀድሞው አትሆንም፤ ለእርሱም ደግሞ እሰጣታለሁ::" '

[28]"አንተ የሰው ልጅ ሆይ! እንዲህ ብለህ ተናገር፤ 'ስለ አሞናውያንና ስለ ስድባቸው ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

" 'ሰይፍ! ሰይፍ!
ሊገድል የተመዘዘ፣
ሊያጠፋ የተጠረገ፣
እንደ መብረቅ ሊያብረቀርቅ
የተወለወለ፤
[29]የታለመልህ የሐሰት ራእይ፣
የተነገረልህ የውሸት ሟርት ቢኖርም፣
የግፍ ጽዋቸው በሞላ፣
ቀናቸው በደረሰ፣
መታረድ በሚገባቸው ክፉዎች፣
አንገት ላይ ይሆናል::
[30]ሰይፉን ወደ ሰገባው መልሰው፤
በተፈጠርህበት ምድር፣
በተወለድህበትም አገር፣
በዚያ እፈርድብሃለሁ::
[31]መዓቴን በላይህ አፈሳለሁ፤
የቍጣዬንም እሳት አነድብሃለሁ፣
በጥፋት ለተካኑ፣
ለጨካኞች ሰዎች አሳልፌ እሰጥሃለሁ::
[32]ለእሳት ማገዶ ትሆናለህ፣
ደምህ በምድርህ ይፈሳል፣
ከእንግዲህ መታሰቢያ አይኖርህም፤
እኔ *እግዚአብሔር* ተናግሬአለሁና::' "

## የኢየሩሳሌም ኀጢአት

**22** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ አትፈርድባትምን? ደም በምታፈሰው በዚህች ከተማ ላይ አትፈርድባትምን? ጸያፍ ተግባሯን ፊት ለፊት ንገራት፤ [3]እንዲህም በላት፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "በመካከልሽ ደምን በማፍሰስና ጣዖታትን በመሥራት ራስሽን የምታረክሺ፣ ፍርድንም በራስሽ ላይ የምታፈጥኚ ከተማ ሆይ፤ [4]ባፈሰስሽው ደም በድለሻል፤ በሠራሽውም ጣዖት ረክሰሻል፤ ከዚህም የተነሣ ቀንሽን አቅርበሻል፤ ዕድሜሽንም አሳጥረሻል:: ስለዚህ ለአሕዛብ መዘባበቻ፣ ለአገሩም ሁሉ መሣለቂያ አደርግሻለሁ:: [5]አንቺ የተዋረድሽና ሽብር የሞላብሽ ሆይ፤ በቅርብም በሩቅም ያሉ ይሣለቁብሻል::

[6]" 'እነሆ በመካከልሽ ያለ እያንዳንዱ የእስራኤል መስፍን ደም ለማፍሰስ ሥልጣኑን ይጠቀማል:: [7]አባቶችና እናቶች በውስጥሽ ተዋረዱ፤ መጻተኞች ተጨቈኑ፤ ድኻ አደጎችና መበለቶች ተንገላቱ:: [8]ንዋያተ ቅድሳቴን አቃለልሽ፤ ሰንበታቴንም አረከስሽ:: [9]ደምን ለማፍሰስ ወሬ የሚያቀብሉ በውስጥሽ አሉ፤ በኰረብታ ቤተ ጣዖት የተሠዋውን የሚበሉና ዝሙትን የሚፈጽሙ ሰዎች በመካከልሽ ይገኛሉ:: [10]የአባታቸውን መኝታ የሚደፍሩ ሰዎች በውስጥሽ አሉ፤ በሥርዐቱ መሠረት ንጹሕ ባልሆኑበት በወር አበባቸው ጊዜ ሴቶችን በማስገደድ የሚደፍሩ በመካከልሽ ይገኛሉ:: [11]በውስጥሽ አንዱ የባልንጀራውን ሚስት ያባልጋል፤ ሌላውም የልጁን ሚስት ያስነውራል፤ ሌላው ደግሞ የገዛ እኅቱ የሆነችውን የአባቱን ልጅ ይደፍራል:: [12]በመካከልሽ ያሉ ሰዎች ደም ለማፍሰስ ጉቦ ይቀበላሉ፤ አንቺም ዐራጣና ከፍተኛ ወለድ+ በመውሰድ ከባልንጀራሽ የማይገባ ትርፍ ዘረፍሽ፤ እኔንም ረስተሻል፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::

[13]" 'ያለ አግባብ ባገኘሽው ጥቅምና በመካከልሽ ባፈሰስሽው ደም ላይ እጄን አጨበ

21+27 ዘፍ49+10፤ መዝ2+6፤ኤር23+5-6፤ሕዝ 37+24፤ ሐጌ2+21-22
21+28 ዘፍ19+38፤ ኤር12+12፤ሶፎ2+8
21+29 ሰቈ25፤ ኤር27+9፤ ሕዝ22+28፤35+5
21+30 ሰቈ5፤ ኤር47+6፤ሕዝ16+3
21+31 መዝ18+15፤ 79+6፤ኢሳ11+4፤ ኤር4+7፤51+20-23፤ ሕዝ16+39፤ 22+20-21
21+32 ሕዝ20+47-48፤25+10፤ ሚል4+1
22+2 ሕዝ16+2፤ 23+36፤24+6፤ ሆሴ4+2፤ናሆ3+1፤ ዕን2+12
22+3 ሰቈ6:13:27፤ ሕዝ23+37:45፤24+6
22+4 2ነገ21+16፤ መዝ44+13-14፤ 137+3፤ሕዝ5+14፤ 21+25
22+5 ኢሳ22+2
22+6 ሕዝ11+6፤ 18+10፤33+25
22+7 ዘፀ22+21-22፤23+9፤ዘዳ5+16፤ ሚክ7+6
22+8 ዘፀ20+8፤ ሕዝ23+38-39
22+9 ዘሌ19+16፤ ኢሳ59+3፤ሕዝ11+6፤ 18+11፤23+29፤ ሆሴ4+2:10:14፤6+9
22+10 ዘሌ12+2፤ 18+7:8:9
22+11 ዘፍ11+31፤ ዘሌ18+9:15፤ 2ሳሙ13+14፤ ኤር5+8፤ሕዝ18+6
22+12 ዘፀ18+21፤ ዘሌ19+13፤ዘዳ27+25፤ መዝ26+10፤ 106+21፤ኢሳ5+23፤ 17+10፤57+11፤ ሕዝ11+6፤18+8፤ አሞ5+12፤ሚክ7+3
22+13 ሰቈ3:27፤ ዘኍ24+10፤ኢሳ33+15፤ ሕዝ6+11፤21+17

+12 ወይም *ዐራጣና ወለድ*

(ዘፀ28+36-37፤ 29+6፤ 39+31፤ ዘሌ8+9) ካህናት በራሳቸው ላይ ይጠመጥሙታል (ዘፀ28+4:37:39፤ 29+6፤ 39+28:31፤ ዘሌ8+9፤ 16+4):: የሚሠራውም በቀጭኑ ከተፈተለ ሐር ነው (ዘጸ28+39፤ 39+28 ይመ):: *የተዋረደው ከፍ ይላል፤ ከፍ ያለውም ይዋረዳል፤* እግዚአብሔር በነገሮች መካከል ጣልቃ በሚገባበት ጊዜ፣ ሁኔታዎች እንደ ሚለዋወጡ የሚያመለክት የተለመደ መጽሐፍ ቅዱሳዊ አገላለጽ ነው (17+24፤ 1ሳሙ2+7-8፤ ሉቃ1+52-53 ይመ)::

21+27 *ባድማ! ባድማ! ባድማ፤* ሦስት ጊዜ ተደጋግሞ መጻፉ አጽንዖትን ለማመልከት ነው (ኢሳ6+3፤ ኤር7+4 ይመ):: *የሚገባው ባለ መብት እስከሚመጣ ድረስ፤* መሲሑን ለማመልከት ነው፤ ይህም ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ ዘፍ49+10 የሚገልጽ ሳይሆን አይቀርም (በዚያ ያለውን ማብ ይመ):: ወይም ደግሞ ናቡከደነፆርን ለማመልከት የገባ ሊሆን ይችላል (2ነገ25+6)::

21+28 *አሞናውያን፤* ሰቈ20 ይመ:: በኢየሩሳሌም ላይ ፍርድ ከተፈጸመባት በኋላ፣ የሚቀጥለው ፍርድ በሌሎች ላይ ይሆናል (ከኢሳ10+5 ጋር ያነጻጽሩ):: *ስለ ስድባቸው፤* 25+3:6 ይመ፤ ከ36+15 ጋርም ያነጻጽሩ:: *ሰይፍ፣ ሰይፍ፤* የናቡከደነፆርን ማለት ነው (ሰቈ9:19 እና ማብ ይመ)::

21+29 *የሐሰት ራእይ ... የውሸት ሟርት፤* ሰላምን በተመለከተ አሞናውያንም እንዲዚሁ የራሳቸው የሆኑ የሐሰት ነቢያት እንዳሉአቸው የታወቀ ነው (የሰቈ10 እና ማብ 13+10፤ ኤር 6+14፤ 8+11-12 ይመ)::

21+30 *ሰይፉን ... መልሰው፤* መልእክቱ ለናቡከደነፆር ነው::

21+31 *ጨካኞች ሰዎች፤* የምሥራቅ ሕዝብ ናቸው በ25+4 ላይ እንዳለው ማለት ነው::

22+2 *በዚህች ከተማ፤* የሕዝቅኤል ትንቢት ያነጣጠረባት ኢየሩሳሌም ናት (5+5 ይመ):: *አትፈርድባትምን?* ከ20+4 ጋር ያነጻጽሩ::

22+3 *ደምን በማፍሰስና ጣዖታትን በመሥራት፤* በዚህ ቦታ ሁለት የኀጢአት ዐይነቶች ተጠቅሰዋል፤ እነዚህም ማኅበራዊ ኢፍትሐዊነትና የጣዖት አምልኮ ናቸው:: *ጣዖታት፤* የ6+4 ማብ ይመ::

22+6 *የእስራኤል መስፍን፤* ነገሥታቱን ሳይሆን፣ በአጠቃላይ መሪዎችን ማለት ነው:: 21+12 ከ19+1 ጋር ያነጻጽሩ::

22+7 *ድኻ አደጎችንና መበለቶች ተንገላቱ፤* ከኢሳ1+17 ጋር ያነጻጽሩ::

22+8 *ሰንበታቴንም፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ልዩ ትኩረት የተሰጠው፣ ሌላው ዐቢይ ጕዳይ ነው (የ20+12 ማብ ይመ)::

22+9 *በኰረብታ ቤተ ጣዖት የተሠዋውን የሚበሉና ዝሙትን የሚፈጽሙ፤* የ6+3፤ 16+15፤ 18+6 ማብ ይመ::

22+10 *ሴቶችን በማስገደድ፤* ከ18+6 ጋር ያነጻጽሩ::

22+11 *ያባልጋል፤* በዚህ ቍጥር ላይ የተጠቀሱት ኀጢአቶች በሙሉ፣ በሕጉ መሠረት በአጽንኦት የተከለከሉ ናቸው (ዘሌ18+7-20፤ 20+10-21፤ ዘዳ22+22-23:30፤ 27+22)::

22+13 *እጄን አጨበጭባለሁ፤* በቍጣ ማለት ነው (21+14:17 ይመ)::

ጭባለሁ። [14]እኔ ልቀጣሽ በምነሣበት ጊዜ በልብ ሙሉነት መቆም ትችያለሽን? ወይስ እጅሽ ሊበረታ ይችላልን? እኔ *እግዚአብሔር* ተናግሬአለሁ፤ አደርገዋለሁም። [15]በሕዝቦች መካከል እበትንሻለሁ፤ በየአገሩም እዘራሻለሁ፤ ርኵሰትሽም አጠራሻለሁ። [16]በሕዝቦች ዘንድ በምትረክሺበት ጊዜ፣[ሀ] እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቂያለሽ።' "

[17]*የእግዚአብሔርም ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ*፤ [18]"የሰው ልጅ ሆይ፤ የእስራኤል ቤት የብረት ጕድፍ ሆነብኝ፤ ሁሉም በከውር ውስጥ ቀልጦ እንደሚቀር መዳብ፣ ቈርቈሮ፣ ብረትና እርሳስ ናቸው፤ እነዚህ ከብር የሚወጡ ጕድፍ ናቸው። [19]ስለዚህ ልዑል *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፣ 'ሁላችሁም የብረት ጕድፍ ስለ ሆናችሁ ወደ ኢየሩሳሌም እሰበስባችኋለሁ። [20]ሰው ብርንና መዳብን፣ ብረትንና እርሳስን እንዲሁም ቈርቈሮን ለማቅለጥ በከውር ውስጥ አስገብቶ እሳት እንደሚያነድበት፣ እኔም እንደዚሁ በቍጣዬና በመዓቴ ወደ ከተማዪቱ እሰበስባችኋለሁ፤ በዚያም አቀልጣችኋለሁ። [21]ሰብስቤአችሁ የቍጣዬን እሳት በእስትንፋሴ አነድባችኋለሁ፤ እናንተም በዚያ ውስጥ ቀልጣችሁ ትቀራላችሁ፤ እኔ *እግዚአብሔር* ቍጣዬን በላያችሁ እንዳፈሰስሁ ታውቃላችሁ። [22]ብር በከውር ውስጥ እንደሚቀልጥ፣ እናንተም በከተማዋ ውስጥ ትቀልጣላችሁ፤ በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* ቍጣዬን በላያችሁ እንዳፈሰስሁ ታውቃላችሁ።' "

[23]*የእግዚአብሔርም ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ*፤ [24]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ምድሪቱን፣ 'አንቺ ያልነጻሽ በቍጣም ቀን ዝናብ ያላገኘሽ[+] ምድር ነሽ' በላት። [25]*መሳፍንቷ*[‡] እያገሣ ግዳዩን እንደሚቦጫጭቅ አንበሳ በውስጧ ያሤራሉ፤ ሕዝቡን ይበላሉ፤ ንብረትንና የከበሩ ነገሮችን ይነጥቃሉ፤ ብዙዎችንም ሴቶች መበለት ያደርጋሉ። [26]ካህናቷ በሕጌ ላይ ያምፃሉ፤ ንዋያተ ቅድሳቴን ያረክሳሉ፤ የተቀደሰውን ከረከሰው አይለዩም፤ በጐደፈውና በንጹሑ መካከል ልዩነት እንደሌለ ያስተምራሉ፤ ሰንበታቴን ከማክበር ዘወር ብለዋል፤ በዚህም በመካከላቸው ተንቄአለሁ። [27]በውስጧ የሚገኙ መኳንንቷ ግዳይ እንደሚቦጫጭቁ ተኵላዎች ናቸው፤ በግፍ ትርፍ ለመሰብሰብ ደም ያፈሳሉ፤ ሕይወትም ያጠፋሉ። [28]ነቢያቷም በሐሰት ራእይና በውሸት ሟርት ይህን ሁሉ ድርጊት ያድበሰብሱላቸዋል፤ *እግዚአብሔርም* ሳይናገር፣ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል' ይላሉ። [29]በምድሪቱ የሚኖረው ሕዝብ ይቀማል፤ ይዘርፋል፤ ፍትሕ በማጕደልም ድኻውንና ችግረኛውን ይጨቍናል፤ መጻተኛውንም ይበድላል።

[30]"ምድሪቱን እንዳላጠፋት ቅጥሩን የሚጠግን፣ በፈረሰውም በኩል በፊቴ የሚቆምላት ሰው ከመካከላቸው ፈለግሁ፤ ነገር ግን አንድም አላገኘሁም። [31]ስለዚህ መዓቴን አፈስባቸዋለሁ፤ በጽኑ ቍጣዬም አነዳቸዋለሁ፤ ያደረጉትንም በራሳቸው ላይ እመልሳለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*"።

## ሁለቱ ዘማውያት እኅትማማቾች

**23** *የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ*፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ከአንድ እናት የተወለዱ ሁለት ሴቶች ልጆች ነበሩ፤ [3]ገና በወጣትነታቸው ዘማውያት በመሆን በግብፅ ሳሉ አመነዘሩ፤ በዚያችም ምድር አጐጠጐጤአቸው ተዳበሰ፤ የድንግልናቸውም ጡቶቻቸው በእጅ ተሻሸ። [4]የታላቂቱ ስም ኦሖላ፣ የእኅቷም ኦሖሊባ ነበር፤ ሁለቱም የእኔ ሆኑ፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆችም ወለዱ። ስማቸውም፣ ኦሖላ ሰማርያ ናት፤ ኦሖሊባም ኢየሩሳሌም።

[5]"ኦሖላ የእኔ ሆና ሳለ በእኔ ላይ አመነዘረች፤

22፥14 መዝ76፥7፤ ሕዝ7፥17፤17፥24፤ 24፥14፤ኢል2፥11፤ ናሆ1፥6፤ሚል3፥2
22፥15 ዘሌ26፥33፤ ዘዳ4፥27፤ሕዝ16፥41፤ 24፥11፤ዘካ7፥14
22፥18 መዝ119፥119፤ኢሳ48፥10፤ኤር6፥28-30
22፥19 መዝ119፥119
22፥20 ሆሴ8፥10፤ ሚል3፥2
22፥21 መዝ68፥2፤ ኢሳ40፥7፤ሕዝ21፥31፤ሐጌ1፥9
22፥22 ኢሳ1፥25፤ 64፥7፤ሕዝ7፥8
22፥24 ሕዝ24፥13
22፥25 መዝ22፥13፤ ኤር11፥9፤15፥8፤ 18፥21፤ሆሴ6፥9
22፥26 ቍ8፤ ዘሌ18፥21፤20፥25፤ 1ሳሙ2፥12-17፤ ኤር 2፥8፡26፤ ሕዝ13፥19፤42፥20፤ 44፥23፤ሆሴ 9፥7-8፤ ሶፎ3፥4፤ ሐጌ2፥11-14፤ ሚል2፥7-8
22፥27 ቍ3፡13፤ ዘፍ37፥24፤ኢሳ1፥23፤ ኤር12፥2፤26፥10፤ 51፥13፤ሕዝ11፥6፤ 33፥25፡31፤34፥2-3፤ ሚክ3፥2፡10፤ሶፎ3፥3፤ ማቴ7፥15
22፥28 ሰቆ2፥14፤ 4፥13፤ሕዝ13፥2፡6-7፡ 10፤21፥29
22፥29 ዘፀ22፥21፤ መዝ62፥10፤ኢሳ5፥7
22፥30 መዝ106፥23፤ ኢሳ64፥7፤ኤር5፥1፤ ሕዝ13፥5
22፥31 ዘፀ32፥10፤ ኢሳ30፥27፤ሰቆ4፥11፤ ሕዝ7፥8-9፤16፥43፤ ሮሜ2፥8
23፥2 ኤር3፥7፤ ሕዝ16፥45
23፥3 ዘሌ17፥7፤ ኢያ24፥14፤ መዝ25፥7፤ኢሳ1፥21፤ ሕዝ16፥15
23፥4 ሕዝ16፥46
23፥5 2ነገ16፥7፤ ሆሴ5፥13፤8፥9

[ሀ]16 ወይም *ርስትሽን ለአንቺ በሰጠሁሽ ጊዜ*
[+]24 ከሰብዓ ሊቃናት ጋር ተመሳሳይ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ያልነጻሽ ወይም ያልዘነበብሽ* ይለዋል
[‡]25 ከሰብዓ ሊቃናት ጋር ተመሳሳይ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ነቢያት* ይለዋል

22፥18 *ጕድፍ፤* ኢየሩሳሌም በምድጃ ተመስላ የቀረበችበትን ኢሳ1፥21-26፤ ኤር6፥27-30 ይመ። ሌሎች የመጥራትን አስፈላጊነት ለማመልከት፣ በተምሳሌት መልክ ያቀረቡትን ሕዝቅኤል ፍጹም ጥፋትን ቍልጭ አድርጎ ለማሳየት ተጠቅሞበታል (የ15፥4 ማብ ይመ)።

22፥25 *መሳፍንትዋ፤* ሕዝቅኤል ከቍ18-22 ላይ፣ "ጕድፍ" የሚለውን ቃል በመጠቀም በግልጽ መናገር ጀመረ። የኢየሩሳሌም መሪዎችና ሕዝቡ ሁሉ እዚህ ላይ ተካትተዋል፤ እነርሱም መሳፍንት፣ ካህናት (ቍ26)፣ መኳንንት (ቍ27)፣ ነቢያትና (ቍ28)፣ ሕዝቡ (ቍ29) ናቸው። *እያገሳ ... አንበሳ፤* ከቍ27፤ 13፥4፤ ሶፎ3፥3 ጋር ያነጻጽሩ።

22፥26 *የተቀደሰውን ከረከሰው አይለዩም፤* ይህ የካህናቱ ዋናው ተግባር ነው (44፥23 ይመ)፤ *ሰንበታቴን፤* የቍ8 ማብ ይመ።

22፥28 *ያድበሰብሱላቸዋል፤* 13፥10 እና ማብ ይመ።

22፥29 *በምድሪቱ የሚኖረው ሕዝብ፤* 7፥27 እና ማብ ይመ።

22፥30 *ሰው ... ፈለግሁ፤* ከኢሳ51፥18፤ 59፥16፤ 63፥5 ጋር ያነጻጽሩ። *በፈረሰውም በኩል በፊቴ የሚቆምላት፤* የ13፥5 ማብ ይመ። በሕዝቡና በእግዚአብሔር መካከል ሆኖ መማለድ፣ ከነቢያት አገልግሎት አንዱ ኀላፊነት ይህ ነው (ዘፍ20፥7፤ 1ሳሙ12፥23፤ ኤር37፥3፤ 42፥2)። አንዳንዶች ይህን ኀላፊነት፣ ማስተማርና ሰዎችን ለንስሓ ማብቃት ነው ብለው ይተረጕማሉ ይህን ኀላፊነት (ከ3፥17-21፤ 33፥1-6 ጋር ያነጻጽሩ)።

23፥4 *ኦሖላ፤* ትርጕሙ፣ "የእርስዋ ድንኳን" ማለት ነው። *ኦሖሊባ፤* ማለት "ድንኳኔ በእርስዋ ውስጥ ነው" ማለት ነው። ይህን በኤር3፥6-12 ከተጠቀሱት ከሁለቱ እኅትማማቾች ጋር ያነጻጽሩ። "ድንኳን" የሚለው ቃል፣ የከነዓናውያንን የኵረብታ ማምለኪያ የሚያመለክቡበት ሊሆን ይችላል፤ ከእግዚአብሔር ማደሪያ ጋር ሊነጻጸር ወይም የእስራኤላውያንን የመኖሪያ ድንኳን አመጣጥ ያመለክት ይሆናል፤ ይሁን እንጂ ሕዝቅኤል የእግዚአብሔርን የማምለኪያ ድንኳን ለማመልከት ይህን ቃል አልተጠቀመበትም።

23፥5 *አመነዘረች፤* ይህ ቃል በም16 ላይ እንደ ተገለጸው፣ በጣዖት አምልኮ ማመንዘርን ሳይሆን፣ ከአሕዛብ ጋር የተደረገውን ፖለቲካዊ የቃል ኪዳን ትስስር የሚያመለክት ነው። እዚህ ላይ የቀረበው ሐሳብ ሰላምዋን ጸጥታዋን በተመለከተ እስራኤል በእግዚአብሔር ከመታመን ይልቅ በዓለም የፖለቲካ መድረክ ላይ ወጥታ ለመጫወት በመፈለጓ፣ እግዚአብሔር ክፉኛ ያዘነባት መሆኑን በሥዕላዊ መልክ ቍልጭ አድርጎ ያሳያል። ይህም እንደ ጣዖት አምልኮ ሁሉ ከሃይማኖት ምንዝርና ጋር እኩል ይቈጠራል። *አሦራውያን፤* 2ነገ15፥19 ይመ።

ጠረኞች ከሆኑት ጎረቤቶቿ ከአሦራውያን ውሽሞቿ ጋር ሴሰነች፤ [6]እነርሱም ሐምራዊ የለበሱ፣ ገዦችና አዛዦች፣ ሁሉም መልከ ቀና ጐበዛዝትና ፈጣን ፈረሰኞች ነበሩ:: [7]እርሷ በዝሙት ራሷን ምርጥ ለሆኑት አሦራውያን ሁሉ አሳልፋ ሰጠች፤ አብረዋት ባመነዘሩት ሰዎች ጣዖት ሁሉ ረከሰች:: [8]በግብፅ የጀመረችውን አመንዝራነቷን አልተ ወችም፤ በዚያ ወንዶች በወጣትነቷ ከእርሷ ጋር ተኙ፤ የድንግልናዋን ጡት አሻሹ፤ ፍትወታቸውን አፈሰሱባት::

[9]"ስለዚህ አብራቸው ላመነዘረች ለአሦራውያን ውሽሞቿ አሳልፌ ሰጠኋት:: [10]እነርሱም ዕርቃን አስቀሯት፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆቿን ነጠቋት፤ እርሷንም በሰይፍ ገደሏት፤ በሴቶችም ዘንድ መተረቻ ሆና ቀረች፤ ፍርድም ተፈጸመባት::

[11]"እኅቷ ኦሖሊባ ይህን አይታ ነበር፤ ሆኖም በፍትወቷና በዘማዊነቷ ከእኅቷ የባሰች ብልሹ ሆነች:: [12]ደግሞም ገዦችና አዛዦች፣ ጌጠኛ ልብስ የለበሱ ጦረኞች፣ ፈጣን ፈረሰኞችና፣ ሁሉም መልከ ቀና ከሆኑት አሦራውያን ጐበዛዝት ጋር አመነዘረች:: [13]ይህችም እንደ ረከሰች አየሁ፤ ሁለቱም በአንድ መንገድ ሄዱ::

[14]"በአመንዝራነቷ እየባሰች ሄደች፤ በደማቅ ቀይ ቀለም በግድግዳ ላይ የተቀረጹ የከለዳውያንን[ገ] ወንዶች ምስል አየች፤ [15]እነርሱም ወገባቸውን በቀበቶ የታጠቁና በራሳቸው ላይ ቀንጠልጣይ ያለው ጥምጥም የጠመጠሙ ነበሩ፤ ሁሉም የከለዳውያን[ነ] ተወላጆችና የባቢሎን ሠረገላ አዛዦች ይመስሉ ነበር:: [16]ባየቻቸውም ጊዜ በፍትወት ተቃጠለች፤ ወደ ከላውዴዎን መልእክተኞች ላከችባቸው:: [17]ባቢሎናውያንም መጥተው ወደ ፍቅር መኝታዋ ገቡ፤ በፍትወታቸውም አረከሷት፤ እርሷም በእነርሱ ከረከሰች በኋላ ጠልታቸው ከእነርሱ ዘወር አለች:: [18]ግልሙትናዋን በአደባባይ በፈጸመችና ዕርቃን በገለጠች ጊዜ ከእኅቷ ዘወር እንዳልሁ፣ ጠልቼአት ከእርሷም ዘወር አልሁ:: [19]እርሷ ግን በግብፅ ያመነዘረችበት የወጣትነት ዘመኗ ትዝ እያላት የባሰ ዘማዊት ሆነች:: [20]በዚያም አባለዘራቸው እንደ አህያ፣ የዘር ፍሰታቸውም እንደ ድንጉላ ፈረስ ዘር ፍሰት ከሆነ ውሽሞቿ ጋር አመነዘረች፤ [21]በግብፅ ምድር ጉያሽን የታሸሸበትንና የወጣትነት ጡቶችሽን የተዳበሰሸበትን[ፐ] የኰረዳነትሽን ብልግና ተመኘሽ::

[22]"ስለዚህ፣ ኦሖሊባ ሆይ፤ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ጠልተሻቸው ከእነርሱ ዘወር ያልሽውን ውሽሞችሽን በአንቺ ላይ አስነሣለሁ፤ እነርሱንም ከየአቅጣጫው አመጣብሻለሁ፤ [23]እነርሱም ባቢሎናውያንና ከለዳውያን ሁሉ፣ የፋቁድ፣ የሱሔና የቆዓ ሰዎች፣ ከእነርሱም ጋር አሦራውያን ሁሉ ናቸው:: እነዚህም መልከ ቀና ጐበዛዝት ሲሆኑ፣ ሁላቸውም በፈረስ ላይ የተቀመጡ ገዦችና አዛዦች፣ የሠረገላ አዛዦችና ከፍተኛ ባለ ሥልጣኖች ነበሩ:: [24]እነርሱም የጦር መሣሪያ[ኣ]፣ ሠረገላና ጋሪ በመያዝ፣ ብዙ ሕዝብ ሆነው ይመጡብሻል፤ ትላልቅና መለስተኛ ጋሻ በማንገብና የራስ ቍር በመድፋት በየአቅጣጫው ይሰለፉብሻል፤ እኔም ለፍርድ በእጃቸው አሳልፌ እሰጥሻለሁ፤ በሕጋቸውም መሠረት ይቀጡሻል:: [25]የቅናት ቍጣዬን በአንቺ ላይ አመጣለሁ፤ እነርሱም በአንቺ ላይ በቍጣ ይወጣሉ፤ አፍንጫሽንና ጆሮሽን ይቈርጣሉ፤ ከአንቺ ወገን የተረፉትም በሰይፍ ይወድቃሉ:: ወንዶችና ሴቶች ልጆችሽን ይወስዱብሻል፤ የተረፉትንም እሳት ይበላቸዋል:: [26]ልብስሽን ይገፉሻል፤ ምርጥ ጌጣጌጥሽንም ይወስዱብሻል:: [27]በግብፅ የጀመርሽውን ብልግናና ሴሰኝነት ከአንቺ አስወግዳለሁ፤ አንቺም ዐይንሽን ወደ እነዚህ አታነሺም፤ ከእንግዲህ ግብፅን አታስቢም::

[28]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ 'እነሆ ተጸይፈሻቸው ከእነርሱ ዘወር ላልሽው ለጠላሻቸው አሳልፌ እሰጥሻለሁ:: [29]እነርሱም በጥላቻ ይቀርቡሻል፤ የለፋሽበትንም ሁሉ ይቀሙሻል፤ ከማሕፀን እንደ ወጣሽ ዕርቃንሽን ያስቀሩሻል፤ የሴሰኝነትሽ ኀፍረት ይገለጣል:: ብልግናሽና ገደብ የለሽ ርኵሰትሽ፣ [30]ይህን አምጥተውብሻል፤ ከአሕዛብ ጋር በማመንዘር በጣዖቶቻቸው ረክሰሻልና:: [31]በእኅትሽ መንገድ ስለ ሄድሽ የእርሷን ጽዋ በእጅሽ አስጨብጥሻለሁ::'

23+7 ኢሳ57+8፤ ሆሴ5+3፤6+10
23+8 ዘፀ32+4፤ ሕዝ16+15
23+9 2ነገ18+11፤ ኤር4+30፤ሆሴ11+5
23+10 ኤር42+10፤ ሕዝ16+36:41፤ ሆሴ2+10
23+11 ኤር3+7:8-11፤ሕዝ16+51
23+12 2ነገ16+7-15፤2ዜና28+16፤ ሕዝ16+15:28
23+13 2ነገ17+19፤ ሆሴ12+2
23+14 ኤር22+14፤ሕዝ8+10፤ናሆ2+3
23+15 ኢሳ5+27
23+16 ኢሳ57+9፤ ሕዝ6+9
23+17 ኤር40+9፤ ሕዝ16+29
23+18 መዝ78+59፤ 106+40፤ኢሳ57+8፤ ኤር6+8፤12+8፤ አሞ5+21
23+21 ሕዝ16+26
23+22 ኤር4+30፤ ሕዝ16+37
23+23 ዘፍ11+28፤ 2ነገ20+14-18፤24+2፤ኤር40+9፤50+21
23+24 ኤር39+5-6፤47+3፤ሕዝ26+7:10፤ናሆ2+4
23+25 ቍ47፤ ዘጸ29+20፤ኤር12+9፤ ሕዝ16+38፤ 20+47-48፤24+21
23+26 ኢሳ3+18-23፤ኤር13+22፤ ሕዝ16+39
23+27 ሕዝ16+41
23+28 ኤር34+20
23+29 ዘዳ28+48፤ ኤር13+27፤ ሕዝ16+36፤22+9፤ ሚክ1+11
23+30 መዝ106+37-38፤ ሶፎ3+1
23+31 2ነገ21+13፤ ኤር25+15

[ገ]14 *ወይም የባቢሎናውያን*
[ነ]15 *ወይም የባቢሎናውያን፤* እንዲሁም በቍ16
[ፐ]21 ከሱርስቱ ጋር (በተጨማሪ ቍ3 ይመ) ተመሳሳይ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *በወጣትነት ጡቶችሽ ምክንያት የተዳበሰሸበትን* ይላል
[ኣ]24 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም አይታወቅም

23+8 *በግብፅ፤* ከ20+5-8 ጋር ያነጻጽሩ:: እስራኤል በታሪኳ እምነት በማጉደሏ ትታወቃለች:: ከግብፅ ጋር ስለ ነበራት ግንኙነት ዘፀ17+3፤ ዘኍ11+5:18:20፤ 14+2-4፤ 21+5 ይመ::

23+10 *ዕርቃኗን አስቀሯት፤* ከ722-721 ዓ.ቅ.ክ. ሰማርያ በአሦራዊያን እጅ መውደቋን የሚያመለክት ነው::

23+14 *በግድግዳ ላይ የተቀረጹ ... ወንዶች ምስል፤* የተቀረጸ ምስልን በማየት የዝሙትን ፍላጐት ማነሳሳት ከተፈጥሮ ሥርዐት ውጭ ነው (16+17 እና ማብ ይመ):: *በደማቅ ቀይ ቀለም ... የተቀረጹ፤* ኤርምያስም እንዲሁ በቀይ ቀለም የተቀቡ ጌጣ ጌጦችን ተቃውሞ ነበር (ኤር22+14)::

23+15 *ቀበቶ፤* ይህን በኢሳ 5+27 ላይ ከተገለጸው የአሦር ወታደሮች ከሚጠቀሙበት የጦር ዕቃ ጋር ያነጻጽሩ::

23+20 *አባላዘራቸው፤* የ16+26 ማብ ይመ::

23+23 *ባቢሎናውያንና ከለዳውያን፤* አብዛኛውን ጊዜ እርስ በርሳቸው ይመሳሰላሉ (1+3 እና አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ 12+13 ይመ):: በዚህና በቍ15 ላይ ተለይቶ የቀረበው፣ ምናልባት ከለዳውያን በቅርብ መምጣታቸውን ለማመልከት ይሆናል:: *ፋቁድ፤* ከባቢሎን በስተ ምሥራቅ የሚኖሩ የአራም ሕዝብ ናቸው:: *የሱሔና የቆዓ፤* ሥነ መሠረታቸው የት እንደሆነ የማይታወቁ፣ ከባቢሎናውያን ጋር የወገኑ ናቸው::

23+24 *በሕጋቸውም መሠረት፤* በሕጋቸው መሠረት ጨካኞ ችና አስፈሪዎች ነበሩ (ቍ 25 ይመ)::

23+25 *እሳት፤* የ15+7፤ 20+47 ማብ ይመ::

23+27 *በግብፅ፤* የቍ 8 ማብ ይመ::

23+31 *ጽዋ፤* በእግዚአብሔር ቍጣ የተሞላ ነው፤ ይህን መጠጣትም መሞትን ያስከትላል፤ የምሳሌያዊ አገላለጹንና እድገቱን

[32]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"ሰፊና ጥልቅ የሆነውን ጽዋ፣
የእኅትሽን ጽዋ ትጠጪአለሽ፤
ብዙም ስለሚይዝ ስድብና ነቀፌታ
ትጠግቢአለሽ።
[33]በእኅትሽ በሰማርያ ጽዋ፣
በመፍረስና በጥፋት ጽዋ፣
በስካርና በሐዘን ትሞዪአለሽ።
[34]ትጠጪዋለሽ፤ ትጨልጪዋለሽም፤
ከዚያም ጽዋውን ትሰባብሪዋለሽ፤
ጡትሽንም ትቈራርጪአለሽ፤

እኔ ተናግሬአለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*።

[35]"ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ረስተሽኛል፤ ወደ ኋላም ገሸሽ አድርገሽኛልና የብልግናሽንና የሴሰኝነትሽን ውጤት ትሸከሚአለሽ።'

[36]*እግዚአብሔር* እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ በኦሖላና በኦሖሊባ ትፈርዳለህን? እንግዲያውስ ጸያፍ ተግባራቸውን ንገራቸው። [37]አመንዝረዋል እጃቸውም በደም ተበክሎአልና። ከጣዖቶቻቸው ጋር አመነዘሩ፤ የወለዱልኝን ልጆቻቸውን እንኳ ለእነርሱ መብል ይሆኑ ዘንድ በእሳት ሠውተውላቸዋል።[h] [38]ደግሞም ይህን አደረጉብኝ፤ በዚያኑ ቀን ቤተ መቅደሴን አረከሱ፤ ሰንበታቴንም አቃለሉ። [39]ልጆቻቸውን ለጣዖቶቻቸው በሠዉባት ዕለት ወደ መቅደሴ ገብተው አረከሷት፤ እንግዲህ በቤቴ ውስጥ ያደረጉት እንዲህ ያለውን ነው።

[40]"ከዚህም በላይ ወንዶች ከሩቅ እንዲመጡላቸው መልእክተኛ ላኩ፤ እነርሱም መጡ። አንቺም ገላሽን ታጥበሽ፣ ዐይንሽን ተኵለሽና በጌጣጌጥ ተውበሽ ጠበቅሻቸው። [41]በተዋበ ዐልጋ ላይ ተቀመጥሽ፤ ዕጣኔንና ዘይቴን ያኖርሽበትንም ጠረጴዛ ከዐልጋው ፊት ለፊት አደረግሽ።

[42]"የሚፈነጥዙ ሰዎች ድምፅ በዙሪያዋ ነበር፤ ከሚያውኩ ሰዎች ጋር ከበረሓ የመጡ ሰካራሞች ነበሩ፤ በሴትየዋና በእኅትዋም ላይ አንባር፣ በራሳቸውም ላይ የተዋበ አክሊል አደረጉላቸው። [43]እኔም በአመንዝራነት ሰውነቷ ስላለቀው፣ 'እርሷ ሕይወቷ ይኸው ስለ ሆነ እንደ ዝሙት ዐዳሪ ይጠቀሙባት' አልሁ። [44]እነርሱም ከእርሷ ጋር ተኙ፤ ሰው ከአመንዝራ ሴት ጋር እንደሚተኛ ከእነዚያ ባለጌ ሴቶች፣ ከኦሖላና ከኦሖሊባ ጋር ተኙ። [45]ጻድቃን ግን ለአመንዝራና ለነፍሰ ገዳይ ሴቶች የሚገባቸውን ፍርድ ይፈርዱባቸዋል። አመንዝሮች ናቸውና፤ እጃቸውም በደም ተበክሎአል።

[46]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ሕዝብን ቀስቅሰህ አምጣባቸው፤ ለሽብርና ለዝርፊያም አሳልፈህ ስጣቸው። [47]ሕዝቡ በድንጋይ ይወግራቸዋል፤ በጐዞ ሰይፋቸው ይቈራርጣቸዋል፤ ወንድና ሴት ልጆቻቸውን ይገድላል፤ ቤቶቻቸውንም ያቃጥላል።

[48]" 'ስለዚህ ሴቶች ሁሉ እንዲጠነቀቁና መጥፎ ፈለጋችሁን እንዳይከተሉ፣ ሴሰኝነትን ከምድሪቱ አጠፋለሁ። [49]የሴሰኝነታችሁን ዋጋ ታገኛላችሁ፤ ጣዖት በማምለክ ለፈጸማችሁት ኀጢአት ቅጣት ትሸከማላችሁ፤ በዚያን ጊዜ እኔ ጌታ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ።' "

### የድስቱ ምሳሌ

**24** በዘጠነኛው ዓመት፣ በዐሥረኛው ወር፣ በዐሥረኛው ቀን የ*እግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ይህን ቀን፣ የዛሬውን ዕለት ለይተህ መዝግብ፤ የባቢሎን ንጉሥ ኢየሩሳሌምን በዚህ ቀን ከቦአታልና። [3]ለዚህ ዐመፀኛ ቤት እንዲህ ብለህ ተምሳሌት ተናገር፤ 'ልዑል *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

" 'ብረት ድስት በእሳት ላይ ጣድ፤
ከጣድህም በኋላ ውሃ ጨምርበት።
[4]ሙዳ፣ ሙዳ ሥጋ፣
ምርጥ ምርጡን ቍርጥ ሁሉ፣ ጭንና
ወርቹን ጨምርበት፤
የተመረጡ ዐጥንቶችንም ሙላበት።
[5]ከመንጋው ሙክቱን ውሰድ፤
ዐጥንቱን ለማብሰል ብዙ ማገዶ ከሥሩ
ጨምር፤
ሙክክ እስከሚል ቀቅለው፤
ዐጥንቱም ይብሰል።

23፥32 መዝ44፥13፤ 60፥3፤ኢሳ51፥17፤ ኤር25፥15፤ሆሴ7፥16
23፥33 ኤር25፥15 -16፤ሕዝ12፥19
23፥34 መዝ16፥5፤ ኤር25፥27
23፥35 ዘዳ32፥18፤ 1ነገ14፥9፤2ዜና29፥6 ፤ኢሳ17፥10፤ሕዝ 16፥52
23፥36 ኢሳ58፥1፤ ሕዝ16፥2፤22፥2፤ ሚክ3፥8
23፥37 ሕዝ16፥36
23፥38 ዘሌ15፥31፤ ነህ10፥31
23፥39 2ነገ21፥4፤ ኤር7፥10፤ሕዝ22፥8
23፥40 2ነገ9፥30፤ ኢሳ57፥9፤ኤር4፥30፤ ሕዝ16፥13-19፤ ሆሴ2፥13
23፥41 ዘኍ18፥12፤ አስ1፥6፤ምሳ7፥17፤ ኢሳ57፥9፤65፥3፡11፤ ኤር44፥5፤ ሕዝ41፥22፤44፥16፤ ሚል 1፥7፡12
23፥42 ዘፍ24፥30፤ 2ዜና9፥1፤መዝ73፥5፤ ሕዝ16፥11-12
23፥43 ቍ3
23፥45 ዘሌ20፥10፤ ሕዝ16፥38፤22፥3፤ ሆሴ2፥2፤6፥5
23፥46 ዘዳ28፥25፤ ኤር25፥9፤ሕዝ16፥40
23፥47 ቍ25፤ 2ዜና 36፥17፡19፤ ኤር34፥22
23፥48 ሕዝ16፥41፤ 2ጴጥ2፥6
23 49 ሕዝ7፥4፤ 9፥10፤16፥58፤ 20፥38፤24፥13
24፥1 ሕዝ8፥1፤ 26፥1፤29፥17
24፥2 2ነገ25፥1፤ ኢሳ30፥8፤ኤር39፥1፤ ዕን2፥2
24፥3 ኢሳ1፥2፤ ሕዝ 2፥3፡6፤11፥3፤ 20፥49
24፥4 ሕዝ11፥7
24፥5 ኢሳ34፥12፤ ኤር52፥10፡24-27፤ ሚክ3፥2-3

[h]37 ወይም *የወለዱልኝን ልጆች እንኳ በእሳት ውስጥ አሳለፏቸው*

በተመለከተ፣ መዝ75፥8፤ ኢሳ51፥17፡22፤ ኤር25፥15-29፤ 49፥12፤ ሰቆ4፥21፤ አብ16፤ ዕን2፥16፤ ማቴ20፥22፤ 26፥39፤ ራእ14፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

23፥37 *ልጆቻቸውን ... ሠውተውላቸዋል፤* የ16፥20 ማብ ይመ።

23፥38 *መቅደሴን አረከሱ፤* ም8 ይመ። *ሰንበታቴን፤* የ22፥8 ማብ ይመ።

23፥40 *መልእክተኛ ላኩ፤* ምናልባት በኤር27 ላይ የተገለጸውንና በሴዴቅያስ ዘመን የነበረውን የኢየሩሳሌምን ታላቅ ጉባኤ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል። *ዐይንሽን ተኵለሽ፤* ወንዶችን ለመማረክ ማለት ነው።

23፥41 *ጠረጴዛ ከዐልጋው ፊት ለፊት አደረግሽ፤* ለግብዣ መዘጋጀትን ያመለክታል (ኢሳ21፥5፤ ምሳ9፥2 ይመ)።

24፥1 *በዘጠነኛው ዓመት፣ በዐሥረኛው ወር፣ በዐሥረኛው ቀን፤* ጥር 15 ቀን 588 ዓ.ቅ.ክ. ነው፤ ይህም ሕዝቅኤል የጠቀሰው አራተኛው ቀን ነው (1፥2፤ 8፥1፤ 20፥1 ይመ)።

24፥2 *የዛሬውን ዕለት ለይተህ መዝግብ፤* እግዚአብሔር በኢየሩሳሌም ላይ የሚደርስበትን ለሕዝቅኤል የገለጸበት ነው።

24፥3 *ዐመፀኛ ቤት፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ እስራኤልን የሚኰንን የመጨረሻው ሐረግ ነው (2፥5፡6፡8፤ 3፥9፡26-27፤ 12፥2-3፡9፡25፤ 17፥12 ይመ)። ይህም የኢየሩሳሌም ዐመፅ ብዙ ሳይቈይ እንደሚደመሰስ የሚያሳይ ነው። *ተምሳሌት፤* ከ17፥2፤ 20፥49 ጋር ያነጻጽሩ። *ማብሰያ ብረት ድስት፤* በ11፥3-12 የቀረበው ምስል፤ ቅሬታዎቹ እርስ በርስ የተነጋገሩበት ሲሆን፣ ይህም ፈጽሞ መደምሰስን የሚያሳይ ነው። የማብሰያ ድስት የተባለችውም ኢየሩሳሌም ናት (ከ 11፥3 ጋር ያነጻጽሩ)።

24፥4 *ምርጥ ምርጡን፤* ከምርኮ የተረፉት (በ597ዓ.ቅ.ክ.) ከመልካምነታቸው የተነሣ እንደሆነ የሚያስቡትን የኢየሩሳሌምን ነዋሪዎች ነው (11፥3 እና ማብ ይመ)።

24፥5 *ማገዶ፤* የናቡከደነፆርን ከበባ ያሳካ መሣሪያ ነው።

[6]“ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላልና፤

“ ‘ለዛገችው ብረት ድስት
ዝገቷም ለማይለቅ፣
ደም ላፈሰሰችው ከተማ ወዮላት!
መለያ ዕጣ ሳትጥል
አንድ በአንድ አውጥተህ ባዶ
አድርገው።

[7]“ ‘የሰው ደም በመካከሏ አለ፤
በገላጣ ዐለት ላይ አደረገችው እንጂ፣
ዐፈር ሊሸፍነው በሚችል፣
በመሬት ላይ አላፈሰሰችውም።
[8]ቍጣዬ እንዲነድና ለመበቀል እንዲያመቸኝ፣
ይሸፈንም ዘንድ እንዳይችል፣
ደሟን በገላጣ ዐለት ላይ አፈሰስሁ።

[9]“ ‘ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ
ይላል፤

“ ‘ደም ላፈሰሰችው ከተማ ወዮላት!
እኔም ደግሞ የምትቃጠልበትን ማገዶ
እቈልላለሁ።
[10]ማገዶውን ከምርበት፤
እሳቱን አንድድ፤
ቅመም ጨምረህበት፣
ሥጋውን በሚገባ ቀቅል፤
ዐጥንቱም ይረር።
[11]ጕድፉ እንዲቀልጥ፣
ዝገቱም በእሳት እንዲበላ፣
ባዶው ድስት እስኪሞቅ፣
መዳቡም እስኪግል ከሰል ላይ ጣደው።
[12]ብዙ ጕልበት ቢፈስበትም፣
የዝገቱ ክምር፣
በእሳት እንኳ፣ ሊለቅ አልቻለም።

[13]“ ‘የረከሰሽው በብልግናሽ ነው፤ ቍጣዬ በአንቺ ላይ እስኪፈጸም ድረስ ከእንግዲህ ንጹሕ አትሆኚም፤ ከርኵሰትሽ ላነጻሽ ፈልጌ፣ መንጻት አልወደድሽምና።

[14]“ ‘እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ፤ የም ሠራበትም ጊዜ ደርሶአል፤ ወደ ኋላ አልልም፤ አልራራም፤ አላመነታምም። እንደ መንገድሽና እንደ ተግባርሽ ይፈረድብሻል፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።’ ”

24፥6 ኢዮ6፥27፤ ሕዝ11፥11፤16፥23፤ 22፥2፤ኢሳ3፥3፤ አብ1፥11፤ናሆ3፥10
24፥7 ዘሌ17፥13
24፥11 ኤር21፥10
24፥13 ኢሳ22፥14፤ ኤር6፥28-30፤ ሰቆ1፥9፤ሕዝ16፥42፤ 22፥24፤23፥36-49፤ ሆሴ7፥1፤ዘካ6፥8
24፥14 ዘኍ11፥23፤ ኢዮ27፥22፤ኢሳ3፥11፤ ሕዝ8፥18፤18፥30፤ 22፥14፤36፥19፤ ዘካ8፥14
24፥16 ቍ21፤ መዝ39፥10፤84፥1፤ ኤር13፥17፤16፥5፤ 22፥10፤ሰቆ2፥4
24፥17 ቍ22፤ ዘፀ28፥39፤ ዘሌ13፥45፤ መዝ39፥9፤ኢሳ3፥20፤ 20፥2፤ኤር16፥7
24፥18 ሕዝ12፥7
24፥19 ሕዝ12፥9፤ 37፥18
24፥21 ቍ16፤ ዘሌ26፥19፤26፥31፤ መዝ27፥4፤ኤር7፥14፤ 15፤ሕዝ7፥24፤23፥25፤ ሆሴ9፥12፡16፤ ሚል2፥12
24፥22 ዘሌ13፥45፤ ኤር16፥7
24፥23 ዘፀ28፥39፤ 33፥4፤ዘሌ26፥16፤ መዝ78፥64፤ ኢሳ3፥20፤20፥2
24፥24 ኢሳ20፥3፤ ሕዝ1፥3፤12፥11
24፥25 ዘዳ28፥32፤ መዝ20፥4፤ ኤር11፥22፤ሰቆ2፥4
24፥26 1ሳሙ4፥12፤ ኢዮ1፥15-19

### የሕዝቅኤል ሚስት መሞት

[15]የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [16]“የሰው ልጅ ሆይ፤ የዐይንህ ማረፊያ የሆነውን ነገር በመቅሠፍት እወስ ድብሃለሁ፤ አንተ ግን ዋይታ አታሰማ፤ አታልቅስ፤ እንባህንም አታፍስስ። [17]ድምፅህን ዝቅ አድርገህ በሐዘን እንጕራጕር እንጂ፣ ለሞተው አታልቅስ። ጥምጥምህን ከራስህ አታውርድ፤ ጫማህንም አታውልቅ፤ አፍህ ድረስ አትሸፋፈን፤ የዕዝን እንጀራም አት ብላ።”

[18]እኔም በማለዳ ለሕዝቡ ተናገርሁ፤ ሚስ ቴም ማታውኑ ሞተች፤ በማግሥቱም ጠዋት እንደ ታዘዝሁ አደረግሁ።

[19]ሕዝቡም፣ “ይህን ስታደርግ ለእኛ የም ታስተላልፈው መልእክት ምን እንደ ሆነ አትነግረንምን?” አሉኝ።

[20]እኔም እንዲህ አልኋቸው፤ “የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [21]ለእስ ራኤል ቤት እንዲህ በል፤ ‘ጌታ እግዚ አብሔር እንዲህ ይላል፤ “የኀይላችሁን ትም ክሕት፣ የዐይናችሁ ማረፊያና የልባችሁ ደስታ የሆነውን መቅደሴን አረክሳለሁ። ትታች ኋቸው የሄዳችሁ ወንድና ሴት ልጆቻችሁ በሰይፍ ይወድቃሉ። [22]እኔ እንዳደረግሁም ታደርጋላችሁ፤ አፋችሁ ድረስ አትሸፋፈኑም፤ የዕዝን እንጀራም አትበሉም፤ [23]ጥምጥማች ሁን ከራሳችሁ አታወርዱም፤ ጫማችሁንም አታወልቁም። በኀጢአታችሁ ትመነምና ላችሁ፤ እርስ በርስ ታቃስታላችሁ እንጂ ሐዘን አትቀመጡም፤ አታለቅሱምም። [24]ሕዝቅኤል ምልክት ይሆናችኋል፤ እርሱ እንዳደረገው ታደርጋላችሁ፤ ይህ በሚሆንበት ጊዜ እኔ ጌታ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቃ ላችሁ።’ ”

[25]“አንተም የሰው ልጅ ሆይ፤ ኀይላቸውን፣ ደስታቸውንና፣ ክብራቸውን፣ የዐይናቸው ማረ ፊያና የልባቸው ደስታ የሆኑትን ወንድና ሴት ልጆቻቸውን ጭምር በምወስድባቸው ቀን፣ [26]በዚያን ቀን፣ ያመለጠ ሰው ይህን ወሬ ሊነግርህ ወደ አንተ ይመጣል፤ [27]በዚ

24፥6 *ለዛገችው፤* ኢየሩሳሌም ልትቋቋ የማትችልበትን ሁኔታ ያመለክታል። *መለያ ዕጣ ሳትጥል፤* በ597 ዓ.ቅ.ክ. ላይ ኢየሩሳሌም ከተያዘች በኋላ፣ ባቢሎናውያን ማርከው የሚወስዱአ ቸውን ሰዎች ለመለየት የጣሉትን ዕጣ ሊሆን ይችላል፤ ሆኖም ግን አሁን ማንም ሳይቀር ሁሉም ይማረካሉ። *ደም ላፈሰሰችው ከተማ፤* ከ22፥3 ጋር ያነጻጽሩ።

24፥7 *ደም ... በገላጣ ዐለት ላይ፤* ኢየሩሳሌም ያፈሰሰች ውን የንጹሐኑን ደም ያለ ኀፍረት በገሀድ ማሳየቷን የሚያመለ ክት ነው (ከኢሳ3፥9 ጋር ያነጻጽሩ)። ያልተሸፈነን ደም በተመለ ከተ ዘፍ4፥10፤ ኢዮ16፥18፤ ኢሳ26፥21 ይመ።

24፥8 *ቍጣዬ፤* የእግዚአብሔርን ቍጣ ነው። ኢየሩሳሌም የጀመረችውን (ቍ7) እግዚአብሔር በፍርድ ይፈጽመዋል። ዘፀ8፥32፤ ከዘፀ9፥12 ጋር ያወዳድሩ።

24፥11 *ባዶው ድስት፤* ነዋሪዎችዋ በምርኮ የተወሰዱባት ኢየሩሳሌም በእሳት ትቃጠላለች፤ በመጨረሻም እርሷን ለማጥራት የሚደረገው ሙከራ ከንቱ ይሆናል።

24፥13 *በብልግናሽ፤* 16፥27፤ 22፥9 ይመ።

24፥16 *በመቅሠፍት፤* አጭር ጊዜ ለሞት የሚዳርግ ክፉ ደዌ ነው (ዘፀ9፥14፤ ዘኍ14፥37 ይመ። *የዐይንህ ማረፊያ፤* እጅግ በጣም የሚወደድንና የሚሳሳለትን ነገር የሚገልጽና (ቍ21፡25 ይመ)፤ የአንድን ሰው ሚስት የሚያመለክት ነው።

24፥17 *ጥምጥምህን ከራስህ አታውርድ፤* ሐዘን የደረሰበት ሰው፣ ጥምጥሙን በመፍታት ዐመድ በዐናቱ ላይ መነስነሱ የተለ መደ ነገር ነበር (ኢሳ7፥6፤ 1ሳሙ4፥12 ይመ)። *ጫማህንም አታውልቅ፤* ጫማንም ማውለቅ የሐዘንን መግለጫ ነበር (2ሳሙ 15፥30 ይመ)። *አፍህ ድረስ አትሸፋፈን፤* የኀፍረት (ሚክ3፥7) ወይም ንጹሕ ያለ መሆን ምልክት ነው (ዘሌ13፥45)። *የእዝን እንጀራም፤* የሐዘን ቤት ምግብ ማለት ነው (ኤር16፥7 ይመ)።

24፥19 *ሕዝቡም ...አትነግረንምን? አሉ፤* ሕዝቡ፣ ሕዝቅ ኤል ስላሳየው ሁኔታ ለሦስተኛ ጊዜ የሰጡት ምላሽ ነው (12፥9፤ 21፥7)።

24፥21 *መቅደሴን አረክሳለሁ፤* ናቡከደነፆር መጥቶ እንዲ ያቃጥለው በማድረግ ነው።

24፥24 *ሕዝቅኤል፤* እዚህ ላይ፣ ነቢዩ ራሱን በሦስተኛ መደብ አድርጎ ይናገራል። በሌላ ቦታ የነቢዩ ስም የተጠቀሰው በ1፥3 ብቻ ነው። *ምልክት፤* የ12፥ 6 ማብ ይመ።

24፥26 *ያመለጠ ሰው፤* በ586 ዓ.ቅ.ክ. ከተማረኩት የመጀመ

ያን ቀን አፍህ ተከፍቶ ከእርሱ ጋር ትነጋገራለህ፤ ከዚያም በኋላ እንደ ድዳ አትሆንም፤ ምልክትም ትሆናቸዋለህ፤ እኔም *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።"

## በአሞን ላይ የተነገረ ትንቢት

**25** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ *መጣ*፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ አሞናውያን አድርገህ፣ ትንቢት ተናገርባቸው፤ [3]እንዲህም በላቸው፤ 'የጌታ፣ *እግዚአብሔርን* ቃል ስሙ፤ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "*መቅደሴ* በረከሰ ጊዜ፣ የእስራኤልም ምድር ባድማ በሆነች ጊዜ፣ የይሁዳም ቤት ተማርኮ በተወሰደ ጊዜ፣ 'እሰይ' ብላችኋልና፣ [4]*ለምሥራቅ* ሕዝብ ትገዙ ዘንድ አሳልፌ እሰጣችኋለሁ፤ እነርሱም በመካከላችሁ ይሰፍራሉ፤ ድንኳኖቻቸውንም በዚያ ይተክላሉ፤ ፍሬያችሁን ይበላሉ፤ ወተታችሁንም ይጠጣሉ። [5]*የራባን* ከተማ የግመሎች *መሰማሪያ*፣ አሞንንም የበጎች *መመሰጊያ* አደርጋለሁ፤ በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ።" [6]*ጌታ እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ "በልባችሁ ክፋት ሁሉ፣ በእስራኤል ውድቀት ላይ በመደሰት በእጃችሁ አጨብጭባችኋልና፤ በመዝለልም ጨፍራችኋልና [7]*ክንዴን* በእናንተ ላይ አነሣለሁ፤ በአሕዛብ እንድትበዘበዙ አደርጋለሁ፤ ከሕዝቦች መካከል አውጥቼ፣ ከአገሮችም ለይቼ አጠፋችኋለሁ፤ እደመስሳችኋለሁም። በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ።' "

## በሞዓብ ላይ የተነገረ ትንቢት

[8]"*ጌታ እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ሞዓብና ሴይር፣ "እነሆ የይሁዳ ቤት እንደ ሌሎቹ አሕዛብ ሁሉ ሆነ" ብለዋልና፤ [9]በምድሪቱ ድንበር ላይ ካሉትና ክብሯ ከሆኑት ከተሞች ከቤትየሺሞት፣ ከበአልሜዎንና ከቂርያታይም ጀምሬ የሞዓብን ዐምባ እገልጣለሁ። [10]ሞዓባውያንንም ከአሞናውያን ጋር ይገዙላቸው ዘንድ ለምሥራቅ ሕዝብ አሳልፌ እሰጣቸዋለሁ፤ አሞናውያን በአሕዛብ ዘንድ ከእንግዲህ *መታሰቢያ* አይኖራቸውም። [11]ሞዓብንም እቀጣለሁ፤ በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።' "

## በኤዶም ላይ የተነገረ ትንቢት

[12]"*ጌታ እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ኤዶም የይሁዳን ቤት ተበቅሎአልና፤ በዚህም በደለኛ ሆኖአልና፤ [13]*ጌታ እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ክንዴን በኤዶም ላይ አነሣለሁ፤ ሰዎቹንና እንስሶቻቸውን እገድላለሁ፤ ባድማ አደርጋታለሁ፤ ከቴማንም ጀምሮ እስከ ድዳን ድረስ በሰይፍ ይወድቃሉ። [14]በሕዝቤ በእስራኤል አማካይነት ኤዶምን እበቀላለሁ፤ እነርሱም እንደ ቍጣዬና እንደ *መዓቴ* መጠን በኤዶም ሕዝብ ላይ ያደርጋሉ፤ ኤዶማውያንም በቀሌን ያውቃሉ፤ ይላል *ጌታ እግዚአብሔር*።' "

24፥27 ሕዝ3፥26፤ 33፥22፤ሉ1፥10፥15
25፥2 ኤር49፥1-6፤ ሕዝ13፥17፤21፥28፤ 29፥2
25፥3 መዝ35፥21፤ ምሳ17፥5፤ሕዝ26፥2፤ 36፥2፤ሶፎ2፥8
25፥4 ዘፍ25፥6፤ ዘኍ31፥10፤ ዘዳ28፥33፡51፤ መሳ6፥3፡33
25፥5 ዘዳ3፥11፤ ኢሳ17፥2
25፥6 ዘኍ24፥10፤ ሕዝ6፥11፤አብ1፥12፤ ሶፎ2፥8
25፥7 ቍ13-14፡17፤ ዘኍ14፥3፤ ሕዝ21፥31፤ አሞ1፥14-15፤ሶፎ1፥4
25፥8 ዘፍ14፥6፤ 19፥37፤ዘዳ23፥6፤ ኢሳ16፥6
25፥9 ዘኍ32፥3፡ 37፤33፥49፤ ኢሱ13፥17፡19
25፥10 ሕዝ21፥32
25፥11 ኢሳ15፥9፤ 16፥1-14፤ኤር48፥1፤ አሞ2፥1-3
25፥12 2ሳሙ8፥ 13-14፤2ዜና28፥17፤ ኢሳ11፥14
25፥13 ዘፍ36፥11፡ 15፡34፤ዘፀ7፥5፤ ኤር 25፥23፤49፥10፤ ሕዝ14፥17፤16፥27፤ 29፥8
25፥14 መዝ137፥7፤ ሕዝ32፥29፤35፥2

---

ሪያውን ማለት ነው። *ወሬ፤* ኢየሩሳሌም በተከበበችበት ጊዜ፣ አጀማመሩና ፍጻሜው እንዴት እንደ ነበረች የሚያሳይ ትክክለኛ (ቍ1-2)፣ ማብራሪያ ነው። (የ33፥21 ማብ ይመ)።

24፥27 *እንደ ድዳ አትሆንም፤* ቤተ መቅደሱ በተቃጠለ ዕለት (በነሐሴ 14 ቀን 586 ዓ.ቅ.ክ.) የሕዝቅኤል ሚስት ሞተች (2ነገ25፥8-9 ይመ)፤ የ3፥26፤ 33፥21 ማብ ይመ። *ምልክት፤* የ12፥6 ማብ ይመ።

25፥1-32፥32፤ በነቢያት አማካይነት በእስራኤል ላይ ተደጋግሞ የሚነገረው የእግዚአብሔር የፍርድ ቃል፣ በአሕዛብ ላይ ከሚደርሰው የፍርድ ንግር ጋር አብሮ የተያያዘ ነው። ይህን ደግሞ ግልጽ የሚያደርገው ነገር ቢኖር፣ "ፍርድ ከእግዚአብሔር ቤት ሲጀምር" (1ጴጥ4፥17)፣ ጣዖት አምላኪ የሆኑ አሕዛብ ከእግዚአብሔር ፍርድ እንደማያመልጡ ነው። አብዛኛውን ጊዜ እንዲህ ዐይነቱ ፍርድ እስራኤልን ወደ እግዚአብሔር የሚመልስ በጥቅል የተነገረ የማዳን መልእክት ሲሆን (28፥25-26 ይመ)፣ በጨካኝ ኀይሎች ላይ የሚገኘውም የእግዚአብሔር ድል የሕዝቡን ጠላቶች ያስወግድላቸዋል፤ እነዚህን ጠላቶች፣ በሕዝቡ ላይ ስላደረሱት ጥፋት ይቀጣቸዋል። እንዲህ ያሉ ንግሮች በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ሰባት ጊዜ ተነግረዋል። ሰባተኛው ንግርም ሰባት ክፍሎች ሲኖሩት፣ እያንዳንዱም፣ "የእግዚአብሔር ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ" የሚል መግቢያ አለው (የመጽሐፉን አስተዋጽኦ ይመ)።

25፥2 *ፊትህን ... አድርገህ፤* የ20፥46፤ ማብ ይመ። *አሞናውያን፤* የዛሬውን የዮርዳኖስን ግዛት በከፊል የሚይዝ ሲሆን፣ ከእስራኤል በስተ ምሥራቅ ያለ ምድር ነው (21፥20 ይመ እንዲሁም ኤር9፥26፤ 49፥1-6፤ አሞ1፥13-15፤ ሶፎ2፥8-11 ይመ)። አሞናውያን በዚያን ጊዜም ሆነ ከዚያ በኋላ ስለ ሠሩት ክፋት 2ነገ24፥2፤ ነህ4፥7 ይመ።

25፥3 *እሰይ፤* እያረሩ መሣቅ ማለት ነው (ከ26፥2፤ 36፥2፤ መዝ35፥21-25 ጋር ያነጻጽሩ)።

25፥4 *ለምሥራቅ ሕዝብ፤* ከአሞን በስተ ምሥራቅ ባለው ምድረ በዳ የሚኖሩትን ዘላኖች የሚያመለክት ይመስላል፤ ይሁን እንጂ ይህ የሚገልጸው ናቡከደነፆርንና ሰራዊቱን ነው (21፥31 ይመ)።

25፥5 *ራባ፤* የ21፥20 ማብ ይመ። *መሰማሪያ ... መመሰጊያ፤* የተደመሰሱ ከተሞች የሚገለጹበት በብሉይ ኪዳን ውስጥ የሚገኝ የተለመደ አባባል ነው (ኢሳ34፥13-15፤ ሶፎ 2፥13-15)። ይህ ቦታ ከተሞች ከመመሥረታቸው በፊት ወደ ነበሩባቸው ሁኔታዎች መመለሳቸው የሰው ጥረት እንዲሁ ከንቱ እንደ ሆነ የሚያመለክት ነው።

25፥6 *በእጃችሁ አጨብጭባችኋልና፤* 6፥11 እና ማብ ይመ።

25፥7 *ክንዴን በእናንተ ላይ አነሣለሁ፤* የ6፥14 ማብ ይመ። *በአሕዛብ እንድትበዘበዙ፤* ከ26፥5፤ 34፥28 ጋር ያነጻጽሩ። *አጠፋችኋለሁ፤* ከቍ16 ጋር ያነጻጽሩ።

25፥8 *ሞዓብ፤* ከአሞን ቀጥሎ በደቡብ በኩል፣ ከሙት ባሕር በስተ ምሥራቅ ያለ ምድር ነው (ኢሳ15-16፤ ኤር48፤ አሞ 2፥1-3፤ ሶፎ2፥8-11 ይመ)። *ሴይር፤* ከሞዓብና ከሙት ባሕር በስተ ደቡብ የሚገኝ ምድር ነው፤ ኤዶም ተብሎም ይጠራል (35፥15፤ 36፥5፤ ኢሳ34፥5-17፤ 63፥1-6፤ ኤር49፥7-11፤ አሞ 1፥11-12 ይመ)። *እንደ ሌሎቹ አሕዛብ ሁሉ፤* እስራኤል እንደ ሌሎቹ አሕዛብ ለመሆን ፈለገች (20፥32 እና ማብ ይመ)፤ አሕዛብም በይሁዳ ላይ ያንዣበበውን የመከራ ደመና ባዩ ጊዜ ለእርሷ የነበራቸውን ፍርሃትና አክብሮት ተዉ፤ ለአምላኳም የቀም ነገር ቦታ ሊሰጡት አልፈለጉም (ከሰቆ4፥12 ጋር ያነጻጽሩ)።

25፥9 *የሞዓብን ዐምባ፤* ከኢየሩሳሌም ሆኖ ማየት የሚቻለው፣ ከሙት ባሕር ጋር የተያያዙትን ዝቅተኞቹን ኮረብቶች፣ ማለት ነው። *ቤት የሺሞት፤* በሞዓብ ሜዳ ላይ ያለ ከተማ ነው። *በኣል ሜዎን፤* ለሞዓብ ንጉሥ ለሜሻ በተሠራ ሐውልት ላይ ስሟ ተቀርጾ የተገኘ የሞዓብ ዋና ከተማ ናት። *ቂርያታይም፤* እንደ በኣልሜዎን ሁሉ በሚሻ ሐውልት ላይ ተቀርጾ ይገኛል (ከ2 ነገ 3፥4-5 ጋር ያነጻጽሩ)።

25፥12 *ኤዶም፤* የቍ8 ማብ ይመ። *ተበቅሎአልና፤* ከ586 ዓ.ቅ.ክ. የይሁዳን ምርኮኞች እንዲወሰዱ በማድረጉ ነው (አብ11-14 ይመ)።

25፥13 *ቴማን፤* በመካከለኛው ኤዶም ከፔትራ አጠገብ የሚገኝ ወረዳ ነው (ኤር49፥7፡20፤ አሞ1፥12፤ አብ9፤ ዕን3፥3 ይመ)። *ድዳን፤* በደቡባዊ ኤዶም የሚገኝ ነገድና ምድር ነው

### በፍልስጥኤም ላይ የተነገረ ትንቢት

[15]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ፍልስጥኤማውያን በቂም ተነሣሥተው በክፉ ልብ ተበቅለዋልና፣ ይሁዳንም በቈየ ጠላትነት ለማጥፋት ፈልገዋልና፤ [16]ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ክንዴን በፍልስጥኤማውያን ላይ አነሣለሁ፤ ከሊታውያንንም እቈርጣለሁ፤ በባሕሩ ጠረፍ ላይ የቀሩትንም አጠፋለሁ:: [17]በታላቅ በቀል እበቀላቸዋለሁ፤ በመዓቴም እቀጣቸዋለሁ፤" በምበቀላቸውም ጊዜ፣ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::' "

### በጢሮስ ላይ የተነገረ ትንቢት

**26** በዐሥራ አንደኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ቀን፣ *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ! ጢሮስ ስለ ኢየሩሳሌም፣ 'እሰይ! የሕዝቦች በር ተሰበረች፤ ደጆቿም ወለል ብለው ተከፈቱልኝ፤ እንግዲህ እርሷ ስለ ፈራረሰች እኔ እከብራለሁ' ብላለችና፤ [3]ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ጢሮስ ሆይ፤ እነሆ በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤ ባሕር ሞገዷን እንደምታስነሣ፣ ብዙ ሕዝብ አስነሣብሻለሁ:: [4]የጢሮስን ቅጥሮች ያወድማሉ፤ ምሽጎቿንም ያፈርሳሉ:: ዐፈሯን ከላይዋ ጠርጌ የተራቈተ ዐለት አደርጋታለሁ:: [5]እኔ ልዑል *እግዚአብሔር* ተናግሬአለሁና፤ በባሕር ውስጥ የመረብ ማስጫ ቦታ ትሆናለች፤ አሕዛብም ይበዘብዟታል፤ [6]መኻል አገር ያሉ ሰፈሮቿም በሰይፍ ይወድማሉ፤ በዚያን ጊዜ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::

[7]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ 'የነገሥታት ንጉሥ የሆነውን፣ የባቢሎንን ንጉሥ ናቡከደነፆርን[a] ከፈረሶችና ከሠረገሎች ጋር፣ ከፈረሰኞችና ከታላቅ ሰራዊትም ጋር ከሰሜን በጢሮስ ላይ አመጣለሁ:: [8]እርሱ መኻል አገር ያሉ ሰፈሮችሽን በሰይፍ ያወድማቸዋል፤ በዙሪያሽ ካብ ይክባል፤ እስከ ቅጥሮችሽ ጫፍ ድረስ ዐፈር ይደለድልብሻል፤ ጋሻውንም በአንቺ ላይ ያነሣል:: [9]ግንብ መደርመሻውን በቅጥሮቿ ላይ ያነጣጥራል፤ በመሣሪያም ምሽጎችሽን ያፈርሳል:: [10]ከፈረሶቹ ብዛት የተነሣ ዐቧራ ይሸፍንሻል፤ ሰዎች ቅጥሮችዋ ወደ ፈረሱ ከተማ እንደሚገቡ እርሱ በበሮችሽ በሚገባበት ጊዜ፣ ከፈረሶቹና ከጋሪዎቹ፣ ከሠረገሎቹም ድምፅ የተነሣ ቅጥሮችሽ ይናወጣሉ:: [11]መንገዶችሽ ሁሉ በፈረሶቹ ኮቴ ይረጋገጣሉ፤ ሕዝብሽን በሰይፍ ይገድላል፤ ታላላቅ ምሰሶዎችሽ ወደ ምድር ይወድቃሉ:: [12]ሀብትሽን ይዘርፋሉ፤ ሸቀጥሽን ይበዘብዛሉ፤ ቅጥሮችሽን ያፈርሳሉ፤ የተዋቡ ቤቶችሽን ያወድማሉ፤ ድንጋይሽን፣ ዕንጨትሽንና የግንቦች ፍርስራሽ ወደ ባሕር ይጥላሉ:: [13]ዘፈንሽን ጸጥ አደርጋለሁ፤ ከእንግዲህም የበገናሽ ድምፅ አይሰማም:: [14]የተራቈተ ዐለት አደርግሻለሁ፤ የመረብ ማስጫ ቦታ ትሆኛለሽ፤ እንደ ገናም ተመልሰሽ አትሠሪም እኔ *እግዚአብሔር* ተናግሬአለሁና፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::'

-3:11፤36+5፤አሞ1+11፤አብ1+1:10-16፤ሚል1+4
25+15 ኢሱ13+3፤2ዜና28+18፤መዝ73+8
25+16 1ሳሙ30+14፤2ዜና26+6፤ሕዝ20+33፤አሞ1+8
25+17 ዘፀ6+2፤8+22፤ዘኍ31+3፤ኢሳ11+14፤14+30፤ኤር44+13፤47+7፤ኢል3+4
26+1 ሕዝ24+1፤29+1፤30+20
26+2 ኢሱ19+29፤2ሳሙ5+11፤ሕዝ25+3
26+3 ቍ19፤ኢሳ5+30፤ኤር50+42፤51+42
26+4 ኢሳ23+1:11፤አሞ1+10
26+5 ዘኍ14+3፤ሕዝ27+32፤29+19፤47+10፤ዘካ9+2-4
26+7 ዕዝ7+12፤ኤር27+6፤39+1፤ሕዝ23+24፤ናሆ2+3-4
26+8 ኤር6+6፤33+4
26+9 ሕዝ21+12
26+10 ኤር4+13፤46+9፤23+24
26+11 ኢሳ5+28፤26+5፤ኤር43+13
26+12 ኢሳ23+8፤ኤር4+7፤ሕዝ27+3-27፤28+8፤ዕን1+8
26+13 ኢዮ30+31፤መዝ137+2፤ኢሳ14+11፤23+7፤ኤር7+34፤16+9፤25+10፤ራእ18+22
26+14 ኢዮ12+14፤ሚል1+4

[a]7 በዕብራይስጥ *ናቡከደነፆር* የሚለው ቃል አማራጭ ትርጉም *ናቡከነፆር* ነው፤ በዚህ ክፍልና በአብዛኛው በሕዝቅኤልና በኤርምያስ መጽሐፍ ውስጥ እንደዚሁ ነው

(27+20፤ 38+13፤ ኢሳ21+13፤ ኤር49+8 ይመ)::

25+15 *ፍልስጥኤማውያን፤* ከይሁዳ በስተ ምዕራብ በሜዲትራኒያን ባሕር ጠረፍ ላይ የሚገኙ ነዋሪዎች ናቸው (1ሳሙ6+17)፤ ንጉሥ ዳዊት ድል እስካደረጋቸው ድረስ፣ ከነዓንን ለመያዝ ብዙ ሲጥሩ ኖረዋል፤ በእስራኤል ላይ የነበራቸውም ጥላቻ፣ ሕዝቡ በምርኮ ወደ ባቢሎን እስከፈለሰ ጊዜ ድረስ እንደ ቀጠለ ነበር (ኢሳ14+29-31፤ ኤር47፤ አሞ1+6-8፤ ሶፎ2+4-7 ይመ)::

25+16 *ከሊታውያን፤* ከፍልስጥኤማውያን ጋር ፍጹም አንድ ባይሆኑም፣ ዝምድና አላቸው (1ሳሙ30+14 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 2ሳሙ8+18፤ 15+18፤ 20+7 ይመ)::

26+1 *በዐሥራ አንደኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ቀን፤* እዚህ ላይ ወሩ መቼ ስንተኛው ወር እንደ ሆነ አልተገለጸም፤ ዘመኑ ግን ከመጋቢት 23 ቀን 587 ዓ.ቅ.ክ. እስከ መጋቢት 13 ቀን 586 ዓ.ቅ.ክ. ባለው ጊዜ ውስጥ ሳይሆን አይቀርም:: ንግሩ የመጣለት በዚህ ዓመት መጨረሻ በ11ኛው (የካቲት 13 ቀን 586 ዓ.ቅ.ክ.) ወይም በ12ኛው ወር (መጋቢት 15 ቀን 586 ዓ.ቅ.ክ.) ነበር ማለት ይቻላል፤ የ33+21 ማብ ይመ:: በትንቢተ ሕዝቅኤል መጽሐፍ፣ ይህ አምስተኛው ቀን ነው (1+2፤ 8+1፤ 20+1፤ 24+1 ይመ)::

26+2 *ጢሮስ፤* የዛሬው የሊባኖስ ግዛት ውስጥ የምትገኝ የቀድሞው የፊንቄ ደሴት ከተማ ናት:: በ594 ዓ.ቅ.ክ. በነበረው በፀረ-አሦራውያን እንቅስቃሴ ውስጥ ተባባሪ ነበረች (ኤር 27+3 ይመ):: ሕዝቅኤል ከማንኛውም ነቢይ ይልቅ በጢሮስ ላይ ትንቢት ተናግሮበታል (ም27-28 ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ23፤ ኤር25+22፤ 47+4፤ ኢዩ3+4-5፤ አሞ1+9-10፤ ዘካ9+2-4 ይመ):: *እሰይ!* የ25+3 ማብ ይመ:: *የሕዝቦች በር፤* መልከዐ ምድራዊ አቀማመጧ በዓለም ዐቀፍ የንግድ እንቅስቃሴ የተጫወተችው ሚናና ፖለቲካዊ ጠቀሜታዋ ጢሮስን፣ "መግቢያ በር" አሰኝቶአታል:: አሦርን ለመቃወም የተደረገው ታላቅ የመሪዎች ስብሰባ የተካሄደውም በዚያ ነበር (ኤር27 ይመ)::

26+3 *በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤* የ5+8 ማብ ይመ:: *ባሕር ሞገድዋን እንደምታስነሣ፤* እዚህ ላይ ወራሪው ሰራዊት በባሕር ሞገድ ተመስሎ ተገልጾአል፤ ከኢሳ17+12-13 ጋር ያነጻጽሩ:: ጢሮአ ደሴት በመሆኗ፣ በተለይ በእዚህ ላይ በተለዋጭ ዘይቤ መገለጹ ተገቢ ነው።

26+5 *አሕዛብም ይበዘብዟታል፤* ከ25+7፤ 34+28 ጋር ያነጻጽሩ::

26+7 *ከሰሜን፤* ናቡከደነፆር ሰራዊቱን ይዞ በመጀመሪያ ወደ አፍራትስ ወንዝ ሽለቆ ከመጣ በኋላ፣ የዐረብን ምድረ በዳ አቋርጦ ከመሄድ ይልቅ የመረጠው አቅጣጫ ቍልቍል ወደ ጢሮስ ይወርዳል (ከኤር1+13 ጋር ያነጻጽሩ):: *ናቡከደነፆር፤* ስሙ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ አራት ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን፣ ይህ የመጀመሪያው ነው (29+18-19፤ 30+10 ይመ):: እርሱም ከ605-562 ዓ.ቅ.ክ. ገዝቶአል፤ የስሙም ትርጒም፣ "አምላኬ ናቡ ሆይ፤ ልጄን ጠብቅ" ወይም "አምላኬ ናቡ ሆይ፤ ድንበሬን ጠብቅ" ማለት ነው:: ይህን አረማዊ ንጉሥ፣ እግዚአብሔር ዐላማውን ለመፈጸም መሣሪያ አድርጎ እንደሚጠቀምበት ኤርምያስና ሕዝቅኤል ገልጸዋል (ኤር25+9፤ 27+6 ይመ):: *አመጣለሁ፤* እግዚአብሔር በአሕዛብ ላይ ያለውን ሥልጣን በግልጽ የሚያመለክት ነው (ከ28+12፤ 29+8 ጋር ያነጻጽሩ)::

26+8 *በዙሪያሽ ካብ ይክባል፤* ናቡከደነፆር የጢሮስን ዙሪያ ለመሥራት ዐሥራ አምስት ዓመት የፈጀበት ሲሆን፣ ሥራውን የጀመረው ግን፣ ኢየሩሳሌም ከወደቀች ከጥቂት ጊዜ በኋላ ነው፤ ሆኖም ጢሮስ በዚህ ጊዜ ስለመያዟ የተጻፈ ማስረጃ አልተገኘም (ኤር25+9፤ 27+6 ይመ)::

26+14 *እንደ ገናም ተመልሰሽ አትሠሪም፤* ብዙም ሳይቆይ፣ ታላቁ እስክንድር በ332 ዓ.ቅ.ክ. በያዛት ጊዜ ይህ ተፈጽሞአል (የኢሳ23+1 ማብ ይመ)::

[15]"ጌታ *እግዚአብሔር* ጢሮስን እንዲህ ይላል፤ 'የቈሰሉት ሲያቃስቱ፣ በውስጥሽም ጭፍጨፋ ሲካሄድ፣ ከውድቀትሽ ድምፅ የተነሣ ደሴቶች አይነዋወጡምን? [16]የባሕር ጠረፍ መሳፍንት ሁሉ ከዙፋኖቻቸው ይወርዳሉ፤ መጐናጸፊያቸውን ይጥላሉ፤ ወርቀ ዘቦ ልብሳቸውን ያወልቃሉ:: ፍርሀት ተከናንበው በመሬት ላይ በመቀመጥ ባለማቋረጥ እየተንቀጠቀጡ በአንቺ ላይ በደረሰው ነገር ይሸበራሉ፤' [17]ስለ አንቺም እንዲህ ብለው ሙሾ ያወርዳሉ፤

"በባሕር ሰዎች የሚኖሩብሽ፣
ባለዝናዋ ከተማ ሆይ፤ እንዴት ጠፋሽ!
ከነዋሪዎችሽ ጋር፣
የባሕር ላይ ኀያል ነበርሽ፤
በዚያ በሚኖሩትም ሁሉ ዘንድ
የተፈራሽ ነበርሽ::
[18]አሁን በመውደቂያሽ ቀን፣
በጠረፍ ያሉ አገሮች ተናወጡ፤
ከመፍረስሽም የተነሣ፤
በባሕር ውስጥ ያሉ ደሴቶች ተደናገጡ::'

[19]"ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'ሰው እንደማይኖርባቸው ከተሞች ባድማ ሳደርግሽ፣ የውቅያኖስንም ውሃ በላይሽ አድርጌ በቀላይ ስሸፍንሽ፣ [20]የጥንት ዘመን ሰዎች ወደ ገቡበት ጕድጓድ ከሚወርዱት ጋር አወርድሻለሁ፤ ወደ ጕድጓድ ከሚወርዱት ጋር በጥንቱ ፍርስራሽ ከምድር በታች አኖርሻለሁ፤ ከዚህም በኋላ በሕያዋን ምድር ተመልሰሽ ቦታ አታገኚም፤[a] [21]መጨረሻሽን አሳዛኝ አደርጋለሁ፤ ከእንግዲህም አትኖሪም፤ ትፈለጊያለሽ፤ ከቶም አትገኚም፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::'"

**ለጢሮስ የወጣ ሙሾ**

**27** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ስለ ጢሮስ ሙሾ አውርድ፤ [3]በባሕር መግቢያ ላይ ለምትገኘውና በብዙ ጠረፎች ከሚኖሩ ሕዝቦች ጋር ለምትነግደው ለጢሮስ እንዲህ በላት፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤

"'ጢሮስ ሆይ!፤
"ፍጹም ውብ ነኝ" ብለሻል፤
[4]ዳርቻሽ በባሕር መካከል ነው፤
ሠሪዎችሽም ፍጹም ውብ አድርገውሻል::
[5]ሳንቃዎችሽን ሁሉ፣
ከሳኔር[b] በመጣ ጥድ ሠሩ፤
ደቀልንም ይሠሩልሽ ዘንድ፤
ከሊባኖስ ዝግባ አመጡ::
[6]ከባሳን በመጣ ወርካ፣
መቅዘፊያሽን ሠሩ፤
ከቆጵሮስ[c] ጠረፍ በመጣ ዝግባ፣[d]
በዝሆን ጥርስ ለብጠው ወለልሽን ሠሩ::
[7]የመርከቦችሽ ሸራ ጥልፍ ሥራ ያለበት
የግብፅ በፍታ ነበረ፤
ይህም እንደ ዐርማ አገለገለሽ::
መጋረጃዎችሽ ከኤሊሳ ጠረፍ የመጡ፣
ባለ ሰማያዊና ሐምራዊ ቀለም ነበሩ::
[8]ቀዛፊዎችሽ ከሲዶናና ከአራድ የመጡ
ነበሩ፤
ጢሮስ ሆይ፤ የራስሽ ጠቢባን የመርከቦችሽ
መሪዎች ነበሩ::
[9]ልምድ ያካበቱ የጌባል[e] ባለሙያዎች፣
መርከብሽን ለመገጣጠም በመካከልሽ
ነበሩ፤
የባሕር መርከቦችና መርከበኞቻቸው ሁሉ፣
ከአንቺ ጋር ሊገበያዩ ይመጡ ነበር::
[10]" 'የፋርስ፣ የሉድና የፉጥ ሰዎች፣

[a]20 ከሰብዓ ሊቃናት ጋር ተመሳሳይ ሲሆን በዕብራይስጡ ግን *ተመላሽ፤ ክብርን እሰጣለሁ* ይላል
[b]5 ሄርሞንን ማለት ነው
[c]6 ዕብራይስጡ *ኪቲም* ይለዋል
[d]6 በታርጕምም እንዲሁ ሲሆን የማሶሬቱ መጽሐፍ የድምፅ ተቀባዮች ፊደል አከፋፈል ግን የተለየ ነው
[e]6 ባይብሎስ ማለት ነው

26+15 ኢዮ24+12፤ ኢሳ41+5፤ኤር49+21፤ ሕዝ27+35
26+16 ዘፀ26+36፤ ዘሌ26+32፤ኢዮ2+8፡ 13፡8+22፤ሕዝ32+10
26+17 ኢሳ14+12፤ ሕዝ19+1
26+18 መዝ46+6፤ ኢሳ23+5፤41+5፤ ኤር49+21፤ሕዝ27+35
26+19 ቍ3፤ ዘፍ7+11፤ኢሳ8+7-8
26+20 ዘኍ16+30፤ ኢዮ28+13፤ መዝ 28+1፤88+6፤ ኢሳ14+9-10፤ ሕዝ31+14፤32+18፤ አሞ9+2፤ዮና2+2፡6
26+21 ኤር20+4፤ 51+64፤ሕዝ27+36፤ 28+19፤ዳን11+19፤ ራእ18+21
27+2 ሕዝ19+1
27+3 ቍ33፤ መዝ 83+7፤ኢሳ23+9፤ ሕዝ16+15፤ሆሴ9+13
27+4 ሕዝ28+12
27+5 ዘዳ3+9፤ ኢሳ2+13
27+6 ዘፍ10+4፤ ዘኍ21+33፤ መዝ29+9፤ ኢሳ23+12፤ ኤር22+20፤ ዘካ11+2
27+7 ዘፍ10+4፤ ዘፀ25+4፤26+36፤ ኢሳ19+9፤ኤር10+9
27+8 ዘፍ10+18፤ 1ነገ9+27
27+9 ኢሱ13+5፤ መዝ104+26
27+10 ዘፍ10+6፤ 2ዜና36+20፤ዕዝ1+1፤ ኢሳ66+19፤ ሕዝ30+5፤38+5፤ ዳን8+20፤ናሆ3+9፤ ማሕ4+4

26+16 *የባሕር ጠረፍ መሳፍንት፤* በ27+35 ላይ ነገሥታት ተብለው ተጠርተዋል፤ ምናልባትም እነዚህ መሳፍንት፣ ከጢሮስ ጋር የጋራ የንግድ ሥራ የነበራቸው ሳይሆኑ አይቀርም:: *መጐናጸፊያቸውን ይጥላሉ፤* ሐዘንተኞች ልብሳቸውን መቅደድ የተለመደ ነገር ነበር (ኢዮ2+12)፤ ይህን ከነነዌ ንጉሥ ድርጊት ጋር ያነጻጽሩ (ዮና3+6):: *ፍርሀት ተከናንበው፤* እንዲህ ካለች ኀያል ከተማ አወዳደቅ የተነሣ የሚፈጠረውን ፖለቲካዊ አለመረጋጋት የሚያመለክት ነው (ከ7+27፤ መዝ 35+26፤ 109+29 ጋር ያነጻጽሩ)::

26+17 *ሙሾ፤* የ19+1 ማብ ይመ::

26+19 *የውቅያኖስ ... ቀላይ፤* በዘፍ 1 ላይ የተገለጸው ዐይነት ባዶና አንዳች ያልነበረበት በጨለማ የተዋጠው "ጥልቅ" ማለት ነው:: የጢሮስም በባሕር ውስጥ ሰጥሞ መቅረት፣ ከዚሁ ሁኔታ ጋር ይመሳሰላል::

26+20 *ወደ ጕድጓድ፤* ወደ መቃብር ማለት ነው (ከመዝ 69+15 ጋር ያነጻጽሩ):: *የጥንት ዘመን ሰዎች፤* ጥንት የሞቱትን ሰዎች ነው (መዝ143+3፤ ሰቆ3+6):: *በሕያዋን ምድር ተመልሰሽ ቦታ አታገኝም፤* ለእስራኤል እንደሚደረገው አይደረግላችሁም ለማለት ነው (37+1-14 ይመ)::

26+21፤ 27+36፤ 28+19 ይመ::

27+2 *ሙሾ፤* የ19+1 ማብ ይመ::

27+3 *ፍጹም ውብ ነኝ፤* 28+12 ይመ፤ ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነውን የትዕቢት አነጋገር ከ28+2 ጋር ያነጻጽሩ:: በሚቀጥሉት ቍጥሮች ጢሮስ፣ "የመንግሥታት መርከብ" ተብላ ስለ ተገለጸች፣ "አንቺ በውበትሽ ልዩ የሆንሽ መርከብ ነሽ" በማለት አንዳንዶች ይተረጕማሉ::

27+4 *ፍጹም ውብ አድርገውሻል፤* ቍ11 ይመ::

25+5 *ሳኔር፤* አሞራውያን የአርሞንዔሞን ተራራ የሚጠሩበት ስም ነው፤ ከሊባኖስ ማዶ ያለ ተራራ ነው::

27+6 *ባሳን፤* የ39+18 ማብ ይመ:: *ቆጵሮስ፤* የተያዘችው በደቡባዊ ቆጵሮስ የምትገኝ ፊንቄያውያን የቅኝ ግዛት ያደረጓት ከተማ ነበረች፤ እርሷም በዕብራይስጥ ኪቲም (አማራጭ ትርጕሙን ይመ) ትባላለች::

27+7 *ኤሊሳ፤* ከቆጵሮስ በስተ ምሥራቅ ትገኛለች፤ የዚች ከተማ ስም የቆጵሮስ ጥንታዊ መጠሪያ ነበር (ሆኖም የዘፍ10+4 ማብ ይመ)::

27+8 *ሲዶና፤* ከጢሮስ በስተ ሰሜን በኩል አርባ ኪሎ ሜትር ርቃ የምትገኝ የባሕር ዳርቻ ከተማ ናት፤ አንዳንድ ጊዜም በንግድም ሆነ በፖለቲካ፣ ከጢሮስ ጋር ትወዳደር ነበር (የ28+21 ማብ ይመ):: *አራድ፤* ከሜዲትራኒያን ጠረፍ ማዶ፣ ከሲዶን በስተ ሰሜን የምትገኝ የነበረች ሌላዋ የፊንቄ ደሴት ከተማ ናት::

27+9 *ጌባል፤* በሲዶናና በአራድ መካከል ባለው ጠረፍ ላይ የምትገኝ ቢብሎስ የምትባል የጥንት ከተማ ናት (አማራጭ ትርጕሙን እና 1ነገ 5+18 ይመ)::

27+10 *ሉድ፤* በትንሹ እስያ የምትገኝ አገር ናት:: *ፉጥ፤* በሰሜን አፍሪካ ከግብፅ በስተ ምዕራብ የምትገኝ ሲሆን፣ እርሷም

ወታደር ሆነው በሰራዊትሽ ውስጥ
አገለገሉ፤
ሞገስም ይሆኑሽ ዘንድ፣
ጋሻቸውንና የራስ ቍራቸውን
በግድግዳሽ ላይ ሰቀሉ።
[11]የአራድና የሔሌክ ሰዎች፣
ቅጥርሽን በየአቅጣጫው ጠበቁ፤
የገማድ ሰዎችም፣ በምሽግሽ ውስጥ ነበሩ።
ጋሻቸውንም በቅጥርሽ ዙሪያ ሰቀሉ፤
ውበትሽንም ፍጹም አደረጉ።

[12]“ ‘ከሀብትሽ ብዛት የተነሣ፣ ተርሴስ ከአንቺ ጋር የንግድ ልውውጥ ታደርግ ነበር፤ ብርና ብረት፣ ቈርቈሮና እርሳስ አምጥታ ሸቀጥሽን ትለውጥ ነበር።

[13]“ ‘ያዋን፣ ቶቤልና ሞሳሕ ከአንቺ ጋር ይነግዱ ነበር፤ ባሪያዎችንና የናስ ዕቃዎችን በሸቀጥሽ ይለውጡ ነበር።

[14]“ ‘የቤት ቴርጋማ ሰዎችም መጋዣዎችን፣ የጦር ፈረሶችንና በቅሎዎችን በሸቀጥሽ ለወጡ።

[15]“ ‘የድዳን ሰዎች ከአንቺ ጋር ተገበያዩ፤ ብዙ የጠረፍ አገሮችም የንግድ ደንበኞችሽ ነበሩ፤ በዝሆን ጥርስና በዞጲ ሸቀጥሽን ይገዙ ነበር።

[16]“ ‘ምርትሽ ብዙ እንደ መሆኑ፣ ሶርያ ከአንቺ ጋር ትገበያይ ነበር፤ ሸቀጥሽንም በበሉር፣ በሐምራዊ ጨርቅ፣ በወርቀ ዘቦ፣ በጥሩ በፍታ፣ በዛጐልና በቀይ ዕንቍ ይለውጡ ነበር።

[17]“ ‘ይሁዳና እስራኤል እንኳ ከአንቺ ጋር ተገበያይተዋል፤ የሚኒትን ስንዴ፣ ጣፋጭ ቂጣ፣ ማር፣ ዘይትና በለሳን በማምጣት በሸቀጥሽ ይለውጡ ነበር።

[18]“ ‘ከሀብት ከንብረትሽ ብዛት የተነሣ፣ ደማስቆ የኬልቦንን የወይን ጠጅና፣ የዛሐርን የበግ ጠጕር በማቅረብ ከአንቺ ጋር ተገበያይታለች።

[19]“ ‘ዌንዳንና ያዋን ከኡሴል መጥተው ከአንቺ ጋር የንግድ ልውውጥ ያደርጉ ነበር፤ ቀልጦ የተሠራ ብረትን፣ ብርጕድንና ቀረፋን በሸቀጥሽ ይለውጡ ነበር።

[20]“ ‘ድዳን ግላስ በማቅረብ ከአንቺ ጋር ትነግድ ነበር።

[21]“ ‘የዐረብና የቄዳር መሳፍንት ሁሉ ደምበኞችሽ ነበሩ፤ ጠቦትና አውራ በግ፣ ፍየልም አምጥተው ከአንቺ ጋር ይገበያዩ ነበር።

[22]“ “የሳባና የራዕማ ነጋዴዎች ከአንቺ ጋር ይገበያዩ ነበር፤ ምርጥ የሆነውን የሽቱ ቅመም ዐይነት ሁሉ፣ የከበረ ድንጋይና ወርቅ በማቅረብ በሸቀጥሽ ይለውጡ ነበር።

[23]“ ‘ካራን፣ ካኔ፣ ዔደን፣ የሳባ ነጋዴዎች፣ አሦርና ኪልማድ ከአንቺ ጋር የንግድ ልውውጥ ያደርጉ ነበር። [24]እነዚህም በገበያሽ ውስጥ ያማረ ልብስ፣ ሰማያዊ ካባ፣ ወርቀ

27፥11 ቍ27
27፥12 ቍ18፡33፤ ዘፍ10፥4
27፥13 ዘፍ10፥2፤ ኢሳ66፥19፤ ሕዝ32፥26፤38፥2፤ 39፥1፤ኢል3፥6፤ ራእ18፥13
27፥14 ዘፍ10፥3
27፥15 ዘፍ10፥7፤ 1ነገ10፥22፤ ኤር25፥22፤ራእ18፥12
27፥16 ዘፀ28፥18፤ 39፥11፤መሳ10፥6፤ ኢዮ28፥18፤ ኢሳ7፥1-8፤ሕዝ16፥10፤ 28፥13
27፥17 ዘፍ43፥11፤ መሳ11፥33፤1ነገ5፥9፤ ሐሥ12፥20
27፥18 ቍ12፤ ዘፍ14፥15፤ ሕዝ47፥16-18
27፥19 ዘፍ10፥2፡ 27፤ዘፀ30፥24
27፥20 ዘፍ10፥7
27፥21 ዘፍ25፥13፤ 2ዜና9፥14፤ ኢሳ21፥17
27፥22 ዘፍ10፥7፡ 28፤43፥11፤ ራእ18፥22
27፥23 ዘፍ10፥22፤ 11፥26፤ዘኍ24፥24፤ ኢሳ37፥12
27፥25 ዘፍ10፥4፤ ኢሳ2፥16፤ራእ18፥3
27፥26 ዘፍ41፥6፤ ኤር18፥17
27፥27 ምሳ11፥4፤ ሕዝ28፥8

15 ከሰብዓ ሊቃናት ጋር ተመሳሳይ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን ዴዳን ይለዋል
16 በአብዛኛዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆችም እንዲሁ ሲሆን አንዳንድ የጥንት የዕብራይስጥ ቅጆችና ሱርስቱ ግን ኤዶም ይላሉ
17 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም አይታወቅም

የዛሬዪቱ ሊቢያ ናት። *ወታደር፤* መርከብነት በመባል ተሰይማ የነበረችው ጢሮስ፣ በዚህ ቍጥር ከተማ ተብላ ተጠርታለች፤ ከዚህም ሌላ አካባቢ ቅጥረኛ ወታደሮች የሚሰበሰቡበት ቦታም ነበረች (በዚህና በሚቀጥለው ቍጥር፣ “ምሽግ” የሚለውን ይመ)።

27፥11 *አራድ፤* የቍ8 ማብ ይመ። *ሔሌክ፤* ከትንሹ እስያ በስተ ደቡብ ምሥራቅ ያለች ኪልቅያ የምትባል ተራራማ አገር ናት። ስሙ በመጽሐፍ ቅዱስ በዚህ ስፍራ ብቻ የሚገኝ ነው። *ገማድ፤* ይህ ስፍራ የትንሹ እስያ ሰሜናዊ ክፍል ነው ወይም ከአራድ አጠገብ የሚገኝ የጠረፍ ከተማ ነው። ይህ ስም በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በሌላ ስፍራ አይገኝም።

27፥12 *ተርሴስ፤* ከስፔን በስተ ደቡብ ባለው ጠረፍ ላይ እንደሚገኝ በዘልማድ ቢነገርም፣ የሰርዲንያ ደሴት ሳይሆን አይቀርም የሚሉ አሉ። 1ነገ10፥22፤ እና በዮና1፥3 ላይ ይህ ስፍራ ከከነዓናውያን ጠረፍ ርቆ የሚገኝ መሆኑ ተጠቅሶአል። ከቍ12-13 ያለው የቦታ ዝርዝር የሚያመለክተው ከምዕራብ ወደ ምሥራቅ ያለውን አቅጣጫ ነው።

27፥13 *ቶቤልና ሞሳሕ፤* ሁለቱም በትንሹ እስያ የሚገኙ አገሮች ናቸው።

27፥14 *የቤት ቴርጋማ፤* ከትንሹ እስያ በስተ ምሥራቅ የምትገኝ አገር ስትሆን፣ እርሷም የዛሬዋ አርሜኒያ ናት (38፥6 ይመ)። *የሥራ መጋዣዎች፤* ትንሹ እስያ በፈረሶች እጅግ የታወቀ አህጉር ነበር (1ነገ10፥28 እና ያንኑ አግራጭ ትርጕም ይመ)።

27፥15 *ድዳን፤* ለኤጅያን ደሴቶች እንደ መግቢያ ሆኖ ሲያገለግል የነበረ፤ ከትንሹ እስያ በስተ ደቡብ ምዕራብ የሚገኝ ትልቅ ደሴት ሲሆን፣ ትልቅ የንግድ ማዕከልም የነበር ነው (ሐሥ 21፥1)።

27፥16 *ሶርያ፤* አራም በመባል ትታወቃለች፤ በቍ18 ላይም ዋና ከተማዋ ደማስቆ መሆኑ ስለተጠቀሰ እዚህ ላይ ኤዶምን የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (አግራጭ ትርጕሙን ይመ፤ 25፥12 እና ማብ ይመ)።

27፥17 *እስራኤል እንኳ ከአንቺ ጋር ተገበያይተዋል፤* ከ722-721 ዓ.ቅ.ክ. ጀምሮ የሰሜኑ የእስራኤል መንግሥት ሕልውናው አብቅቶለት ስለነበር፣ ይህ አባባል የሚያመለክተው ቀደም ያሉትን ዓመታት ሁኔታ ነው። *ሚኒት፤* የአሞናውያን ከተማ ስትሆን፣ ምርጥ በሆነ የስንዴ ምርቷ የምትታወቅ አገር ነበረች። *በለሳን፤* በገለዓድ ከሚገኙት ዕፅዋት ከአንዱ የሚዘጋጅ ሙጫ ወይም የሚቀባ ዘይት ነው፤ (ዘፍ37፥25፤ ኤር8፥22፤ 46፥11)።

27፥18 *ደማስቆ፤* የሶርያ ዋና ከተማ ናት (የቍ16 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ኢሳ7፥8 ይመ)። *ኬልቦን፤* ከደማስቆ በስተ ሰሜን የነበረችና ዛሬም ያለች ከተማ ስትሆን፣ በወይን ጠማቂነቷ ስመ ጥር ናት። በመጽሐፍ ቅዱስ ስሟ የተጠቀሰው እዚህ ላይ ብቻ ነው። *ዛሐር፤* ከደማስቆ በስተ ሰሜን ምዕራብ የምትገኝና ከብቶች የሚግጡባት፣ የዛሬዪቱ ሳሕራ ናት።

27፥19 *ዌንዳ፤* ሆሜር በዚህ ስም ግሪኮችን ጠርቷቸዋል። *ኡሴል፤* ዘፍ10፥27፤ 1ዜና1፥21 ይመ፤ ይህ ቦታ ምናልባትም የመንን ወይም በካራንና በጤግሮስ መካከል ያለውን አገር የሚያመለክት ሊሆን ይሆናል።

27፥20 *ድዳን፤* የ25፥13 ማብ ይመ።

27፥21 *የዐረብና የቄዳር፤* ከሶርያ እስከ ዓረብ ምድረ በዳ ያሉትን ዘላኖች የሚገልጽ አባባል ነው፤ ቄዳርን በተመለከተ ኢሳ 42፥11፤ 60፥7፤ ኤር49፥28 ይመ።

27፥22 *ሳባ፤* የ23፥42 ማብ ይመ። *ራዕማ፤* በደቡብ ዐረብ የምትገኝ ከተማ ናት።

27፥23 *ካራን፤* በዛሬዪቱ ምሥራቃዊ ቱርክ የምትገኝ ከከርከሚሽ በስተ ምሥራቅ ያለች ከተማ ናት፤ ጥንት የንግድ እንዲሁም ሲን ለሚባለው የጨረቃ አምላክ የአምልኮ ማእከል ነበረች፤ አብርሃምም ከዚህ ስፍራ ነበር ወደ ከነዓን የተጓዘው ከዚህ ስፍራ ተነሥቶ ነበር (ዘፍ11፥31፤ 12፥4)። *ካኔ፤* ይህ ቦታ የት እንደ ሆነ በትክክል ባይታወቅም፤ ምናልባት በሜስጶጦምያ የሚገኝ ሊሆን ይችላል፤ አብዛኛውን ጊዜ ከካልኖ ጋር ይመሳሰላል (ኢሳ 10፥9፤ አሞ6፥2)። *ዔደን፤* በ2ነገ19፥12 ከተጠቀሰችው ከካራን ጋር አንድ የሆነችና በስተ ደቡብ የምትገኝ ወረዳ ናት። በአሞጽ 1፥5 የተጠቀሰችውን ቤተ ዔደንን ይመ። *ሳባ፤* የ23፥42 ማብ ይመ። *አሹር፤* ከተማዪቱን፣ አገሩና (አሦርን) ሕዝቡን (አሦራውያንን) የሚያመለክት ነው። *ኪልማድ፤* ከተማ ለመሆኗ በውል አይታወቅም፤ ይሁን እንጂ በመስጴጦምያ ውስጥ የምትገኝ

ዘቦ እንዲሁም በኀብረ ቀለም ያሸበረቀና በጥብቅ የተታታ ስጋጃ በማቅረብ ከአንቺ ጋር ይነግዱ ነበር።

[25]“ ‘የተርሴስ መርከቦች፣
ሸቀጥሽን አጓጓዙልሽ፤
በባሕር መካከልም፣
በከባድ ጭነት ተሞልተሽ ነበር።
[26]ቀዛፊዎችሽ፣
ወደ ጥልቁ ባሕር ይወስዱሻል፤
የምሥራቁ ነፋስ ግን፣
በባሕሩ መካከል ይሰባብርሻል።
[27]የመርከብ አደጋ በሚደርስበሽ ቀን፣
ሀብትሽ፣ ሸቀጥሽና የንግድ ዕቃሽ፣
መርከብ ነጂዎችሽ፣ መርከበኞችሽና
መርከብ ሠሪዎችሽ፣
ነጋዴዎችሽና ወታደሮችሽ ሁሉ፣
በመርከብ ላይ ያሉትም ሁሉ፣
ወደ ባሕሩ ወለል ይዘቅጣሉ።
[28]መርከበኞችሽ ሲጮኹ፣
የባሕሩ ጠረፍ ይናወጣል።
[29]ቀዛፊዎች ሁሉ፣
መርከባቸውን ጥለው ይሄዳሉ፤
መርከብ ነጂዎችና መርከበኞችም ሁሉ፣
ወርደው ባሕሩ ዳር ይቆማሉ፤
[30]ድምፃቸውን ከፍ አድርገው፣
በምሬት ያለቅሱልሻል፤
በራሳቸውም ላይ ዐቧራ ነስንሰው፣
በዐመድ ላይ ይንከባለላሉ።
[31]ስለ አንቺ ጠጕራቸውን ይላጫሉ፤
ማቅም ይለብሳሉ፤
በነፍስ ምሬት፣
በመራራም ሐዘን ያለቅሱልሻል።
[32]ስለ አንቺ በዋይታ ያለቅሳሉ፤
እንዲህም እያሉ ሙሾ ያወርዳሉ፤
“ባሕር ውጦት የቀረ፣
እንደ ጢሮስ ማን አለ?”
[33]ሸቀጥሽ ከባሕር በወጣ ጊዜ፤
ብዙ ሕዝቦችን ታጠግቢ ነበር፣
በታላቅ ሀብትሽና ሸቀጥሽ፣
የምድርን ነገሥታት ታበለጽጊ ነበር።
[34]አሁን ግን በጥልቅ ውሃ ውስጥ፣
በባሕር ተንኰታኵተሻል፤
ጭነትሽና ተሳፋሪዎችሽ ሁሉ፣
ከአንቺ ጋር ሰጥመዋል።
[35]በጠረፍ አገር የሚኖሩ ሁሉ፣
በአንቺ ሁኔታ ተደናግጠዋል፤
ንጉሦቻቸው በፍርሀት ራዱ፤
ፊታቸውም ተለዋወጠ።
[36]በሌሎች ሕዝቦች መካከል ያሉ ነጋዴዎች
ምንኛ አፏጩብሽ!
መጨረሻሽ አስደንጋጭ ሆነ፤
ለዘላለምም አትገኚም።’ ”

## በጢሮስ ንጉሥ ላይ የተነገረ ትንቢት

**28** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ለጢሮስ ገዥ እንዲህ በለው፤ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

“ ‘ልብህ በትዕቢት ተወጥሮ፣
“እኔ አምላክ ነኝ፤
በአምላክ ዙፋን ላይ፣
በባሕሮችም ልብ ተቀምጫለሁ” አልህ።
ምንም እንኳ እንደ አምላክ ጠቢብ ነኝ
ብለህ ብታስብም፣
አንተ ሰው እንጂ አምላክ አይደለህም።
[3]ከዳንኤል[ጦ] ይልቅ ጠቢብ ነህን?
ከአንተስ የተሰወረ ምስጢር የለምን?
[4]በጥበብህና በማስተዋልህ፣
የራስህን ሀብት አከማቸህ፤
ወርቅም ብርም፣
በግምጃ ቤትህ አጠራቀምህ።
[5]በንግድ ሥራ እጅግ ከመራቀቅህ የተነሣ፣
በሀብት ላይ ሀብት አካበትህ፤
ከሀብትህ ብዛት የተነሣም፤
ልብህ በትዕቢት ተወጠረ።
[6]“ ‘ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ
ይላል፤
“ ‘እንደ አምላክ ጥበበኛ ነኝ፤ ብለህ
ስለምታስብ፣
[7]ከአሕዛብ መካከል እጅግ ጨካኞች
የሆኑትን ባዕዳን፣
በአንተ ላይ አመጣለሁ፤
በጥበብህ ውበት ላይ ሰይፋቸውን ይመዛሉ፤
ታላቅ ክብርህንም ያረክሳሉ።
[8]ወደ ጕድጓድ ያወርዱሃል፤
በጥልቁም ባሕር ውስጥ፣
በባሕሮችም ልብ ውስጥ አሰከፊ ሞት
ትሞታለህ።
[9]ታዲያ በገዳዮችህ ፊት፣
“አምላክ ነኝ” ትላለህን?
በገዳዮችህ እጅ ስትገባ፣
አንተ ሰው እንጂ አምላክ አይደለህም።
[10]በባዕዳን እጅ፣
ያልተገረዙትን ሰዎች አሟሟት

[ጦ]3 ወይም ዳኤል፤ የዕብራይስጡን ቃል አጻጻፍ ስንመለከት ነቢዩ ዳንኤልን ሳይሆን ሌላን ሰው የሚያመለክት ነው

27፥28 ኢር49፥21
27፥30 ኢሱ7፥6፤ 2ሳሙ1፥2፤ኢር6፥26፤ ራእ18፥18-19
27፥31 ዘሌ13፥40፤ አስ4፥1፤ኢዮ1፥20፤ 3፥20፤ኢሳ3፥17፤ 16፥9፤22፥12፤ ኢር6፥26፤48፥37፤ ሰቆ2፥10፤ሕዝ7፥18፤ ራእ18፥15
27፥32 ኢሳ23፥1 -6፤ሕዝ19፥1፤26፥5
27፥33 ቍ3፡12፤ ሕዝ28፥4-5
27፥34 ዘካ9፥4
27፥35 ዘሌ26፥32፤ ኢዮ18፥20፤ ሕዝ26፥15፡17-18፤ 32፥10
27፥36 መዝ37፥10፡36፤ ኢር19፥8፤49፥17፤ 50፥13፤ሕዝ26፥21፤ ሶፎ2፥15
28፥2 ዘፍ3፥5፤ መዝ9፥20፤82፥6-7፤ ኢሳ13፥11፤14፥13፤ ሕዝ16፥49፤ሶፎ2፥15፤ 2ተሰ2፥4
28፥3 ሕዝ14፥14፤ ዳን1፥20፤2፥20-23፡ 28፤5፥11-12
28፥4 ኢሳ10፥13፤ ዘካ9፥3
28፥5 ኢዮ31፥25፤ መዝ52፥7፤62፥10፤ ኢሳ23፥8፤ኢር9፥23፤ ሕዝ27፥33፤ ሆሴ12፥8፤13፥6
28፥7 ኢር9፥23፤ ሕዝ7፥24፤30፥11፤ ዕን1፥6
28፥8 መዝ55፥23፤ ሕዝ26፥12፤27፥27፤ 32፥30፤ራእ18፥7
28፥9 ኢሳ31፥3፤ ሕዝ16፥49
28፥10 1ሳሙ14፥6፤ ኢር9፥26፤ ሕዝ32፥19፡24

ሳትሆን አይቀርም።

27፥25 *ተርሴስ፤* የቍ12 ማብ ይመ። ጢሮስ በመርከብ የተመሰለችበት ሁኔታ እንደ ገና እዚህ ላይም ተደግሞአል (የቍ 3፡10 ማብ ይመ)።

27፥26 *የምሥራቁ ነፋስ፤* በባሕርም (መዝ48፥7) ሆነ በመሬት (ኢር18፥17) ላይ ብዙ ጥፋት የሚያደርስ ነው፤ ምናልባትም ናቡከደነፆርን በተአምርት የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (17፥10፤ 19፥12 ይመ)።

27፥30 *በራሳቸውም ላይ ዐቧራ፤* ለተመሳሳይ ሁኔታ 26፥16 ይመ። *በዐመድም ላይ ይንከባለላሉ፤* ከሚክ1፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

27፥31 *ጠጕራቸውን ይላጫሉ፤* ከ7፥18፤ ኢሳ15፥2፤ 22፥12 ጋር ያነጻጽሩ።

28፥2 *ለጢሮስ ገዥ፤* አባባሉ የጢሮስን ከተማ እንደ ገዥ በመቍጠር የተጠቀሰ ወይም በጊዜው የጢሮስ ከተማ ገዥ የነበረውን ኢቶባአልን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ቍ12 ይመ)። *በትዕቢት፤* ከ27፥3፤ ምሳ16፥18፤ ሐሥ12፥21-23 ጋር ያነጻጽሩ።

28፥3 *ዳንኤል፤* የ14፥14 ማብ ይመ።

28፥7 *ባዕዳን፤* ባቢሎናውያንን ነው።

28፥8 *ጕድጓድ፤* ከኢዮ33፥22፡24 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ26፥20 ማብ ይመ።

28፥10 *ያልተገረዙ፤* ይህ አባባል አረማዊነትን ጨካኝነትን

ትሞታለህ፤
እኔ ተናግሬአለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብ
ሔር::' "

[11]የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [12]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ስለ ጢሮስ ንጉሥ ሙሾ አውርድ፤ እንዲህም በለው፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

" 'ጥበብን የተሞላህ፣ ፍጹም ውበትን
የተላበስህ፣
የፍጹምነት ምሳሌ ነበርህ::
[13]በእግዚአብሔር የአትክልት ቦታ፣
በዔድንም[ሠ] ነበርህ፤
እያንዳንዱ የከበረ ድንጋይ አስጊጦህ ነበር፤
ሰርድዮን፣ ቶጳዝዮን፣ አልማዝ፣
መረግድ፣ ኢያስጲድ፣ ሰንፔር፣
በሉር፣ ቢረሌና የከበረ ዕንቍ::[ሰ]
ልብስህም የሚያብረቀርቅ ዕንቍ ወርቅ
ነበር፤
የተዘጋጁትም አንተ በተፈጠርህበት ዕለት
ነበር::
[14]ጠባቂ ኪሩብ ሆነህ ተቀብተህ ነበር፤
ለዚሁም ሾምሁህ፤
በእግዚአብሔር ቅዱስ ተራራ ላይ ነበርህ፤
በእሳት ድንጋዮች መካከል ተመላለስህ::
[15]ከተፈጠርህበት ቀን ጀምሮ፣
ክፋት እስከ ተገኘብህ ድረስ፣
በመንገድህ ነቀፌታ አልነበረብህም::
[16]ንግድህ ስለ ደረጀ፣
በዐመፅ ተሞላህ፣
ኀጢአትም ሠራህ፤
ስለዚህ ከእግዚአብሔር ተራራ በውርደት
አሳደድሁህ፤
ጠባቂ ኪሩብ ሆይ፤ ከእሳት ድንጋዮች
መካከል አስወጣሁህ::
[17]በውበትህ ምክንያት፣
ልብህ ታበየ፤
ከክብርህ ታላቅነት የተነሣም፣
ጥበብህን አረከስህ::
ስለዚህ ወደ ምድር ወረወርሁህ፤
ለነገሥታት ትዕይንት አደረግሁህ::
[18]በኀጢአትህና በተጭበረበረው ንግድህ
ብዛት፣
መቅደስህን አረከስህ::
ስለዚህ እሳት ከአንተ እንዲወጣ አደረግሁ፤
እርሱም በላህ፤
በሚመለከቱህ ሁሉ ፊት፣
በምድር ላይ ዐመድ አደረግሁህ::
[19]የሚያውቁህን አሕዛብ ሁሉ፣
ሁኔታህ አስደንግጦአቸዋል፤
መጨረሻህ የሚያሳዝን ሆነ፤
ከእንግዲህ ሕልውና የለህም::

## በሲዶን ላይ የተነገረ ትንቢት

[20]የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [21]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ ሲዶና አዙር፤ ትንቢትም ተናገርባት፤ [22]እን ዲህም በል፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

" 'ሲዶን ሆይ፤ በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤
በውስጥሽ እከብራለሁ፤
ቅጣትን ሳመጣባት፣
ቅድስናዬንም በውስጧ ስገልጥ፣
እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ
ያውቃሉ::
[23]በእርሷ ላይ መቅሠፍት አመጣለሁ፤
በመንገዶቿ ላይ ደም እንዲፈስ
አደርጋለሁ፤
ከየአቅጣጫው በሚመጣ ሰይፍ፣
የታረዱት በውስጧ ይወድቃሉ፤
ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንኩ
ያውቃሉ::

[24]" 'ከእንግዲህ ወዲያ የእስራኤል ሕዝብ የሚያውቃይ አሜከላና የሚወጋ እሾኽ የሆኑ ጎረቤቶች አይኖሯቸውም፤ ከዚያም እኔ ጌታ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::

28፥12 ሕዝ19፥1፤ 27፥2-4
28፥13 ዘፍ2፥8፤ ኢሳ14፥11፤ ሕዝ27፥16፤31፥8-9፤ ራእ17፥4፤21፥20
28፥14 ዘፀ25፥17-20፤30፥26፤40፥9
28፥16 ዘፍ3፥24፤ 6፥11፤ዕን2፥17
28፥17 ኢሳ10፥12፤ ሕዝ16፥49፤19፥12፤ 31፥10
28፥18 አብ1፥18፤ ዘካ9፥2-4፤ሚል4፥3
28፥19 ዘሌ26፥32፤ ኤር51፥64፤ሕዝ 26፥21
28፥21 ዘፍ10፥15፤ ኤር25፥22፤ሕዝ 13፥17
28፥22 ዘሌ10፥3፤ ሕዝ30፥19፤39፥13
28፥23 ሕዝ5፥17፤ 38፥22
28፥24 ኢሳ5፥6፤ ሕዝ2፥6

[ሠ]13 ወይም ቀፒስ ቀሡሊ
[ሰ]13 ከእነዚህ የከበሩ ድንጋዮች መካከል አንዳንዶቹ ትክክለኛ ማንነታቸው ተለይቶ አይታወቅም

የሚያመለክት ነው፡ ይሁን እንጂ ፊንቄያውያን እንደ እስራኤላውያንና እንደ ግብፃውያን ይገረዙ ነበር (31፥18፤ 32፥19 ይመ)::

28፥12 *ሙሾ፤* የ19፥1 ማብ ይመ:: *ስለ ጢሮስ ንጉሥ፤* ከቍ2 ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም የኢሳ14፥12-15 ያለውን ማብ ይመ:: *የፍጹምነት ምሳሌ፤* "ምሳሌ" ሲል በሐጌ2፥23 ላይ እንደ ተገለጸው የዚህ ትርጕም በቃሉ፣ "ማኅተም" ማለት ነው፤ ሕዝቅኤል በሚሸነቍጥ የምፀት ቃል፣ ትዕቢተኛውን የጢሮስን ንጉሥ በመጀመሪያ የተፈጠረ ሰው፣ በጥበብና በውበት የላቀ አድርጎ አቅርቦታል::

28፥13 *በዔድን ነበርህ፤* እንደ አዳም ማለት ነው (ዘፍ 2፥15):: እዚህ ላይ ነቢዩ ሕዝቅኤል የሰውን አፈጣጠርና ውድቀት ያነሣው፣ የጢሮስን ንጉሥ ዕጣ ፈንታ ሥዕላዊ በሆነ መንገድ ለማሳየት ነው (31፥9፡16፡18):: *እያንዳንዱ የከበረ ድንጋይ፤* (ዘፍ2፥25)፣ ንጉሡ እዚህ ላይ የቀረበው ዕርቃኑን እንደ ነበረው አዳም ሳይሆን የእግዚአብሔርን ቅዱስ ቦታ ለመጠበቅ እንደ ተቀባ ካህን ሙሉ በሙሉ ለብሶ ነው (ዘፀ28፥17-20):: *በተፈጠርህበት ዕለት፤* ከቍ15፤ ዘፍ5፥2 ጋር ያነጻጽሩ::

28፥14 *ጠባቂ ኪሩብ ሆነህ፤* ከቍ16 ጋር ያነጻጽሩ:: አዳምና ሔዋን ከተባረሩ በኋላ ኪሩቤል የዔድንን ገነት ይጠብቁ ነበር (ዘፍ3፥24):: *በእግዚአብሔር ቅዱስ ተራራ፤* ከቍ16 ጋር ያነጻጽሩ:: ይህ ሁኔታ በዘፍጥረት የተጠቀሰውን ታሪክ አያንፀባርቅም፤ እግዚአብሔር መኖሪያውን በተራሮች ላይ ስለማድረጉ ኢሳ 14፥13 ይመ:: *በእሳት ድንጋዮች፤* የከበሩ ድንጋዮችን የሚያመለክት ነው (ቍ13፤ ከራእ4፥1-16፤ 21፥15-21 ጋር ያነጻጽሩ)::

28፥15 *ነቀፌታ አልነበረብህም፤* ይህ በዘፍ2፥3 ላይ ከተገለጸው ጋር ተጓዳኝ መሆኑ ግልጽ ነው (ዘፍ6፥9፤ 17፥1 ይመ)::

28፥16 *ንግድህ ስለ ደረጀ ዐመፅ ተሞላህ፤* የጢሮስ ዋነኛ በደሏ ይህ ነው::

28፥21 *ፊትህን ... አዙር፤* የ20፥46 ማብ ይመ:: *ሲዶን፤* 27፥8 እና ማብ ይመ:: በብሉይ ኪዳን መጽሐፍ ውስጥ፣ ሲዶን ከጢሮስ ተለይታ የተጠቀሰችበት ስፍራ ይህ ብቻ ነው (ከኢሳ 23፥1-4፤ ኤር47፥4፤ ኢል3፥4፤ ዘካ9፥2 ጋር ያነጻጽሩ)::

28፥22 *በአንቺ ላይ ተነሥቻለሁ፤* ምናልባትም ይህ አባባል፣ ሲዶን ኢየሩሳሌምን ለመውጋት በተሰበሰበው ጉባኤ ከተሳታፊት መካከል በመገኘቷ ሊሆን ይችላል (ኤር27፥3፤ የ5፥8 ማብ ይመ):: *በውስጥሽ እከብራለሁ፤* ሲዶን በመቀጣቷ ምክንያት የእግዚአብሔር ክብር ይታወቃል ማለት ነው::

28፥24 *የሚያውቃይ አሜከላ፤* የእስራኤል ጠላቶች እንደ አሜከላ የተመሰሉበትን ዘኍ33፥55፤ ኢሱ23፥13 ይመ::

[25]" 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ የእስራኤልን ሕዝብ ከተበተኑባቸው አገሮች መካከል በምሰበስብበት ጊዜ፣ አሕዛብ እያዩ ቅድስናዬን በመካከላቸው እገልጣለሁ፤ ከዚያም በገዛ ምድራቸው ይኖራሉ፤ ይህም ለባሪያዬ ለያዕቆብ የሰጠሁት ነው። [26]በዚያም በሰላም ይኖራሉ፤ ቤቶች ይሠራሉ፤ የወይን ተክል በታም ያበጃሉ። ያጣጣሏቸው ጎረ ቤቶቻቸውን ሁሉ በምቀጣበት ጊዜ እነርሱ በሰላም ይኖራሉ፤ ከዚያም እኔ *እግዚአብሔር* አምላካቸው እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።' "

## በግብፅ ላይ የተነገረ ትንቢት

**29** በዐሥረኛው ዓመት፣ በዐሥረኛው ወር፣ በዐሥራ ሁለተኛው ቀን የ*እግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ ግብፅ ንጉሥ ወደ ፈርዖን አዙር፤ በእርሱና በግብፅ ሁሉ ላይ ትንቢት ተናገር፤ [3]እንዲህም ብለህ ተናገረው፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል።

" 'በወንዞችህ መካከል የምትተኛ አንተ
ታላቅ አውሬ፣
የግብፅ ንጉሥ ፈርዖን፤ በአንተ ላይ
ተነሥቻለሁ።
"የዐባይ ወንዝ የእኔ ነው፤
ለራሴም ሠርቼዋለሁ" ትላለህ።
[4]ነገር ግን በመንጋጋህ መንጠቆ አስገባለሁ፤
የወንዞችህን ዓሦች ከቅርፊትህ ጋር
አጣብቃለሁ፤
ቅርፊትህ ላይ ከተጣበቁት ዓሦች ሁሉ ጋር፣
ከወንዞችህ ጐትቼ አወጣሃለሁ።
[5]አንተንና በወንዞችህ ያለውን ዓሣ ሁሉ፣
በምድረ በዳ እጥላለሁ።
በገላጣ መሬት ላይ ትወድቃለህ፤
የሚሰበስብህ፣ የሚያነሣህም አይኖርም።
ለምድር አራዊትና ለሰማይ ወፎች፣
ምግብ እንድትሆን አሳልፌ እሰጥሃለሁ።

[6]ከዚያም በግብፅ የሚኖሩ ሁሉ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።

" 'ለእስራኤል ቤት የሸምበቆ በትር ነበርህ፤ [7]በእጃቸው ሲይዙህ ተሰንጥረህ ትከሻቸውን ወጋህ፤ ሲደገፉህም ተሰብረህ ጀርባቸውን አጐበጥ።[a]

[8]" 'ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ሰይፍ አመጣብሃለሁ፤ ሰዎችህንና እንስሶቻቸውን እገድላለሁ። [9]ግብፅ ባድማና ምድረ በዳ ትሆናለች፤ ከዚያም እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።

" 'የዐባይ ወንዝ የእኔ ነው፤ እኔም ሠርቼዋለሁ" ብለሃልና፤ [10]ስለዚህ በአንተ ላይ ተነሥቻለሁ፤ በወንዞችህ ላይ ተነሥቻለሁ፤ የግብፅንም ምድር ከሚግዶል እስከ አስዋን ከዚያም እስከ ኢትዮጵያ ወሰን ድረስ ፍርስራሽና ባድማ አደርጋታለሁ። [11]የሰው እግርም ሆነ የእንስሳ ኮቴ በውስጧ አያልፍም፤ እስከ አርባ ዓመት ማንም አይኖርባትም። [12]የግብፅን ምድር ከጠፉት ምድሮች መካከል እንደ አንዱ ባድማ አደርጋታለሁ፤ ከተሞቿም በፈራረሱት ከተሞች መካከል አርባ ዓመት ባድማ ይሆናሉ፤ ግብፃውያንንም በአሕዛብ መካከል እበትናቸዋለሁ፤ በአገሮችም መካከል እዘራቸዋለሁ።

[13]" 'ያም ሆኖ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ከአርባ ዓመት በኋላ ግብፃውያንን ከተበተኑበት አገሮች መካከል እሰበስባቸዋለሁ። [14]ከተማረኩበት አመጣቸዋለሁ፤ ወደ

28+25 መዝ106+47፤ ኢሳ11+12፤ ኤር12+15፤23+8፤ ሕዝ11+47፤20+41፤ 34+27፤37+25
28+26 ዘሌ25+18፤ ዘዳ20+6፤1ነገ4+25፤ መዝ149+9፤ኢሳ 65+21፤ኤር17+25፤ 32+15፤ሕዝ38+8፤ 39+26-27፤ሆሴ2+15 ፤11+11፤አሞ 9+14-15
29+1 ቍ17፤ሕዝ 26+1
29+2 ኢሳ19+1-17 ፤ኤር25+19፤46+2፤ ሕዝ25+2፤30+1-26፤ 31+1-18፤32+1-32
29+3 መዝ68+30፤ 74+13፤ኤር44+30፤4 6+8፤ሕዝ32+2
29+4 2ነገ19+28፤ ኢዮ41+2፤ሕዝ38+4
29+5 ኤር7+33፤ 8+2፤34+20፤ ሕዝ31 +13፤ 32+4-6፤39+4
29+6 2ነገ18+21
29+7 2ነገ18+21፤ ኢሳ36+6፤ኤር17+5፤ ሕዝ17+15-17
29+8 ሕዝ25+13፤ 32+11-13
29+9 ኤር46+8፤ ሕዝ30+7-8፡13-19
29+10 ዘፀ3+22፤ 14+2፤ኢሳ18+1፤ ኤር 21+13፤46+19፤ ሕዝ 30+4፡6
29+11 ሕዝ32+13
29+12 ኢሳ34+10፤ ኤር46+19፤30+7፡ 23፡26
29+14 ኢሳ11+11፤ 19+22፤ኤር46+26፤ ሕዝ17+14፤30+14

[a]7 በሱርስቱም (በተጨማሪ ሰብዓ ሊቃናትና ቩልጌትን ይመ) እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ጀርባቸውን ቀጥ አደረግህ* ይላል

28+25 *የእስራኤልን ሕዝብ ... በምሰበስብበት ጊዜ፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍና በሌላም ስፍራ ተደጋግሞ የተሰጠ የተስፋ ቃል ነው (11+17፤ 20+34፡41-42፤ 29+13፤ 34+13፤ 36+24፤ 37+21፤ 38+8፤ 39+27፤ ነህ1+9፤ ዘካ10+8፡10 ይመ)። *ለባሪያዬ ለያዕቆብ፤* ከ37+25 ጋር ያነጻጽሩ። ስለ ተሰጠው የተስፋ ቃል ዘፍ28+13፤ 35+12፤ መዝ105+10-11 ይመ።

28+26 *በዚያም በሰላም ይኖራሉ፤* የተስፋውን ቃል ልዩና ትርጕም ያለው የሚያደርግ፣ የማያቋርጥ ሐሳብ ነው (ከ34+28፤ 38+8፡11፡14፤ 39+26፤ ዘሌ25+18-19፤ ኤር23+6፤ 32+37፤ 33+16 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቤቶች ... የወይን ተክል በታ፤* እነዚህ ለጥሩ ኑሮ መሠረታዊ የሆኑ ነገሮች ናቸው (ከኢሳ65+21፤ ኤር 29+5፡28፤ አሞ9+14 ጋር ያነጻጽሩ)።

29+1 *በዐሥረኛው ዓመት፣ በዐሥረኛው ወር፣ በዐሥራ ሁለተኛው ቀን፤* ጥር 7 ቀን 587 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው፤ ይህ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ከተጠቀሱት ቀናት ስድስተኛው ነው (1+2፤ 8+1፤ 20+1፤ 24+1፤ 26+1 ይመ)። ከዚህ በስተቀር በግብፅ ላይ (30+1)፣ ቀን ከተነገሩባት ሰባት ንግሮች ይህ የመጀመሪያው ሲሆን፣ እነዚህም ግብፅ ከፈጸመቻቸው ድርጊቶች ላይ የተወሰዱባትን መለኮታዊና ትንቢታዊ ቅጣት የሚያመለክቱ ናቸው።

29+2 *ፊትህን ... አዙር፤* የ20+46 ማብ ይመ። *ፈርዖን፤* ከ589-570 ዓ.ቅ.ክ. የነበረውን ሖፍራ ማለት ነው (ኤር44+30 ይመ)።

29+3 *በወንዞችህ፤* የዐባይን ወንዝ መፋሰሻና መስኖ ቦዮችን ማለት ነው (ከኢሳ7+18፤ 19+6፤ 37+25 ጋር ያነጻጽሩ)። *ታላቅ አውሬ፤* ወይም "ዐዞ" ማለት ነው፤ ይህም የተገለጸው በዐባይ ወንዝ እንደሚገኝ ነው፤ የዘፀ4+3 ማብ እንዲሁም ኢዮ41+1 እና አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ኢሳ27+1 ይመ። *ትላለህ፤* ይህ የትምክህት ቃል፣ በግብፃውያን ሐውልቶች ላይ ተቀርጾ ይገኛል። *በአንተ ላይ ተነሥቻለሁ፤* የ5+8 ማብ ይመ።

29+4 *መንጠቆ፤* ከ19+4 ጋር ያነጻጽሩ። *የወንዞችህን ዓሦች፤* ግብፅ ያሸነፈቻቸውን ግዛቶች ወይም ቅጥረኛ ወታደሮችዋን የሚያመለክት ነው።

29+5 *ለምድር አራዊት ... ምግብ፤* በፒራሚዶች ላይና በግብፃውያን "የሙታን መጽሐፍ" እንደተገለጸው፣ ፈርዖኖች በምድር ላይ የኖሩትን ዐይነት ሕይወት፣ ከሞት በኋላም እንኖራለን በማለት የሚያልሙትን የዐጕል ተስፋ ከንቱነት የሚገልጽ ነው።

29+6 *የሸምበቆ በትር ነበርከ፤* ቀደም ሲል የተገለጸ ንጽጽር ነው (ኢሳ36+6)። ሖፍራ በአጭሩ ባይሳካለትም፣ ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምን እንዳይከቡ አቅጣጫቸውን አስቀይሮአቸዋል (ኤር 37+1-10 ይመ)።

29+8 *ሰይፍ፤* የናቡከደነፆርን ማለት ነው (የ21+3 ማብ ይመ)። በሌሎች የነቢያት መጽሐፍ ላይ ባይገኝም፣ ጠቅላላ አገላለጹን በተመለከተ 6+3፤ 11+8፤ 14+17፤ 33+2 ይመ፤ እንዲሁም ዘሌ26+25 ይመ።

29+10 *ሚግዶል፤* ይህ ስፍራ የት እንደሆነ በውል አይታወቅም፤ ምናልባት በሰሜናዊ ግብፅ የሚገኝ ሊሆን ይችላል (ኤር44+1፤ 46+14 ይመ)። *አስዋን፤* በደቡብ ግብፅ ያለ ከተማ ነው፤ ከዳን እስከ ቤርሳቤህ የሚለው አገላለጽ መላውን እስራኤል እንደሚያመለክት ሁሉ (መሳ20+1፤ 1ሳሙ3+20) "ከሚግዶል እስከ አስዋን" የሚለው አባባልም (30+6 ይመ) መላውን የግብፅ ምድር የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም።

29+11 *አርባ ዓመት፤* ረጅምና መከራ የበዛበትን አስቸጋሪ ጊዜ የሚያመለክት ነው (ከ4+6 ጋር ያነጻጽሩ)።

አባቶቻቸው ምድር ወደ ጳትሮስ እመልሳቸዋለሁ። [15]ከመንግሥታት ሁሉ አነስተኛ ትሆናለች፤ ከሌሎችም አሕዛብ በላይ ራሷን ከፍ ማድረግ አትችልም። እጅግ ደካማ አደርጋታለሁ፤ ስለዚህ ሌሎችን አሕዛብ እንደ ገና መግዛት አትችልም። [16]ግብፅ ከእንግዲህ ለእስራኤል ሕዝብ መታመኛ አትሆንም፤ ለርዳታ ወደ እርሷ ዘወር ባሉ ጊዜ ያደረጉት ኀጢአት ግን መታሰቢያ ትሆናለች። ከዚያም እኔ ጌታ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።’ ”

[17]በሃያ ሰባተኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [18]“የሰው ልጅ ሆይ፤ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር አስቸጋሪ በሆነ ዘመቻ ሰራዊቱን በጢሮስ ላይ አንቀሳቀሰ፤ የሁሉም ራስ ተመልጦአል፤ የሁሉም ትከሻ ተልጧል፤ ይሁን እንጂ እርሱና ሰራዊቱ በጢሮስ ላይ ካደረጉት ዘመቻ ያተረፉት ነገር የለም። [19]ስለዚህ ልዑል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ግብፅን ለባቢሎን ንጉሥ ለናቡከደነፆር እሰጣለሁ፤ ሀብቷን ሁሉ ያግዛል፤ ለሰራዊቱም ደመወዝ ይሆን ዘንድ ምድሪቱን ይበዘብዛል፤ ይመዘብራልም። [20]እርሱና ሰራዊቱ ለእኔ በመልፋታቸው፣ ግብፅን ለድካሙ ዋጋ ሰጥቼዋለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።

[21]“በዚያ ቀን ለእስራኤል ቤት ቀንድ[a] አበቅላለሁ፤ በመካከላቸውም አፍህን እከፍታለሁ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ።

## ስለ ግብፅ የወጣ ሙሾ

**30** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በል፤ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

“ ‘ዋይ! በል፤ እንዲህም በል፤
“ወዮ ለዚያ ቀን!”

[3]ቀኑ ቅርብ ነው፤
የእግዚአብሔር ቀን ቅርብ ነው፤
የደመና ቀን፣
ለአሕዛብም የጥፋት ቀን ነው።
[4]በግብፅ ላይ ሰይፍ ይሆናል፤
በኢትዮጵያም ላይ ጭንቀት ይመጣል።
የታረዱት በግብፅ ሲወድቁ፣
ሀብቷ ይወሰዳል፤
መሠረቶቿም ይፈርሳሉ።

[5]ኢትዮጵያና ፉጥ፣ ልድያና መላው ዐረብ፣ ሊብያና[b] የቃል ኪዳኑ ምድር ሕዝብ ከግብፅ ጋር በአንድነት በሰይፍ ይወድቃሉ።

[6]“ ‘እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“ ‘የግብፅ ተባባሪዎች ይወድቃሉ።
የምትኰራበት ብርታቷ ይወድቃል።
ከሚግዶል እስከ አስዋን፣
በውስጧ በሰይፍ ይወድቃሉ፤
ይላል ጌታ እግዚአብሔር።
[7]“ ‘በባድማ መሬቶች መካከል፣
ባድማ ይሆናሉ፤
ከተሞቻቸውም፣
ከፈራረሱ ከተሞች መካከል ይሆናሉ።
[8]በግብፅ ላይ እሳት ስጭር፣
ረዳቶቿ ሁሉ ሲደቁ፣
በዚያን ጊዜ እኔ እግዚአብሔር እንደ
ሆንሁ ያውቃሉ፤

[9]“ ‘በዚያ ቀን ከእኔ ዘንድ መልእክተኞች በመርከብ ወጥተው ተዘልላ ከተቀመጠችበት ሁኔታ ለማውጣት ኢትዮጵያን ያስፈራሯታል፤ ግብፅ በጨለማ በምትዋጥበት ቀን ጭንቅ ይይዛቸዋል፤ ቀኑ በእርግጥ ይመጣልና።

[10]“ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“ ‘በባቢሎን ንጉሥ በናቡከደነፆር እጅ፣
ስፍር ቍጥር የሌለውን የግብፅን ሕዝብ
እደመስሳለሁ።

29፥15 ዘካ10፥11
29፥16 ዘኍ5፥15፤ 2ዜና32፥10፤ ኢሳ 20፥5፤30፥2፤ ሰቆ 4፥17፤ሆሴ8፥13
29፥17 ቍ1፤ሕዝ 24፥1፤30፥20፤40፥1
29፥18 ዘፍ49፥15፤ ዘሌ13፥40፤ኢዮ1፥20፤ኤር27፥6፤39፥1፤ 48፥37
29፥19 ኢሳ19፥4፤ ኤር43፥10-13፤ሕዝ 26፥5፤30፥4፡10፡24 -25፤32፥11
29፥20 ኢሳ10፥6 -7፤43፥3፤45፥1፤ኤር 25፥9
29፥21 መዝ132፥17 ፤ሕዝ3፥27፤33፥22፤ ሉቃ1፥69
30፥2 ኢሳ13፥6፤ ያዕ5፥1
30፥3 ቍ18፤ ሕዝ7፥7፡12፡19፤32፥7፤ 34፥12፤ኢል1፥15፤ 2፥1፡11፤አብ1፥15
30፥4 ዘፍ10፥6፤ ኤር25፥19፤ ሕዝ29፥10፡19፤ ዳን11፥43
30፥5 2ዜና9፥14፤ ኤር25፥20፤ ሕዝ27፥10፤ናሆ3፥9
30፥6 ሕዝ29፥10
30፥7 ሕዝ29፥12
30፥8 ኤር49፥27፤ ሕዝ29፥9፤39፥6፤ አሞ1፥4፡7፡10፤ ናሆ1፥6
30፥9 ዘፍ10፥6፤ ኢሳ23፥5፤ ሕዝ32፥9-10፤ ሶፎ2፥12
30፥10 ኤር39፥1፤ ሕዝ29፥19

[a]21 *ቀንድ* በዚህ ቦታ ጥንካሬን ያመለክታል
[b]5 *ዕብራይስጡ ኩብ* ይላል

29፥14 *ጳትሮስ፤* ደቡባዊ ግብፅን ነው (30፥14፤ ኤር 44፥1፡15 ይመ)።

29፥17፤ በግብፅ ላይ የተነገረው ሁለተኛው ንግር ነው (የቍ1 ማብ ይመ)። *በሃያ ሰባተኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ወር በመጀመሪያው ቀን፤* ሚያዝያ 26 ቀን 571 ዓ.ቅ.ክ. ነው፤ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተጠቀሰ ሰባተኛው ቀን ነው (ቍ1፤ 1፥2፤ 8፥1፤ 20፥1፤ 24፥1፤ 26፥1)፤ በዚህ መጽሐፍ የተጠቀሱት ሌሎች ቀናት ከሞላ ጐደል የጊዜን ቅደም ተከተል የጠበቁ ሲሆን፣ እዚህ የተጠቀሰው ይህ ቀን ንግግሩ ግብፅን የሚመለከት በመሆኑ የገባ ሳይሆን አይቀርም።

29፥18 *አስቸጋሪ በሆነ ዘመቻ፤* ናቡከደነፆር ጢሮስን ለዐሥራ አምስት ዓመት ከብቦአታል፤ ይህም የሆነው ከ586-587 ዓ.ቅ.ክ. ነው (26፥7-14 ይመ)። *የሁሉም ራስ ተመልጦአል፤* ከቈዳ የተሠራ የራስ ቍር በማድረጋቸው ሊሆን ይችላል።

29፥19 *እሰጣለሁ፤* እግዚአብሔር ከመንግሥታትና በሕዝቦች ሁሉ ላይ ያለውን የበላይነት በድጋሚ የሚያመለክት ነው።

29፥21 *ቀንድ አበቅላለሁ፤* ኀይሉን እንዲያጠናክር አደርጋለሁ ማለት ነው ምንባቡ ስለ መሲሑ የተነገረ ትንቢት አይደለም። *አፍህን እከፍታለሁ፤* የሕዝቅኤል ድዳነት ያበቃል ማለት ነው (3፥26፤ 24፥27)፤ ይህ ቃል በ33፥22 ላይ የተጠቀሰውን ይመለከታል።

*30፥1፤* በግብፅ ላይ የተነገረ ሦስተኛው ንግር ነው (የ29፥1 ማብ ይመ)፤ እዚህ ላይ ቀኑ ባይጠቀስም፣ በ587 ዓ.ቅ.ክ. ከታኅሣሥ እስከ ጥር ወር ባሉት ቀናት መካከል ሳይሆን አይቀርም፤ 29፥1 ከ30፥20 ጋር ያወዳድሩ። በዚህ ጊዜም ኢየሩሳሌም ተከባ ነበር።

30፥2-3 *ለዚያ ቀን ... የእግዚአብሔር ቀን፤* እግዚአብሔር በፍርድ የሚመጣበት ቀን ማለት ነው (7፥7 እና ማብ ይመ)። በግብፅ ላይ የሚመጣባት ፍርድም በዚህ ጊዜ ተነግሮአል።

30፥3 *ቀኑ ቅርብ ነው፤* ከኢሳ13፥6 ጋር ያነጻጽሩ። *የደመና ቀን፤* ከኢል2፥2፤ ሶፎ1፥15 ጋር ያነጻጽሩ።

30፥4 *ሰይፍ፤* የናቡከደነፆርን ማለት ነው (ቍ10፤ የ21፥3 ማብ ይመ)።

30፥5 *ፉጥ፤* በአፍሪካ አህጉር የምትገኘው ሊብያ ናት (የ27፥10 ማብ ይመ)። *ልድያ፤* በትንሹ እስያ (የ27፥10 ማብ ይመ) የምትገኘው ሳይሆን፣ በሰሜን አፍሪካ ያለችውን አገር ነው። *የቃል ኪዳኑ ምድር ሕዝብ፤* በግብፅ የሚኖሩ አይሁዳውያንን ነው (ኤር44 ይመ)።

30፥6 *ከሚግዶል እስከ አስዋን፤* የ29፥10 ማብ ይመ።

30፥8 *እሳት፤* ጦርነትን ሳስነሣ ማለት ነው።

30፥9 *መልእክተኞች በመርከብ፤* መርከቦች በዐባይ ወንዝ ላይ መጓዛቸውን አስመልክቶ በኢትዮጵያ ላይ ስለተነገረው ንግር ኢሳ 18 ይመ።

[11]ከአሕዛብ ሁሉ እጅግ ጨካኝ የሆኑት፣
 እርሱና ሰራዊቱ፣
 ምድሪቱን ለማጥፋት እንዲመጡ
 ይደረጋል፤
ሰይፋቸውን በግብፅ ላይ ይመዛሉ፤
 ምድሪቱንም ሬሳ በሬሳ ያደርጋሉ፤
[12]የዐባይን ወንዝ ውሃ አደርቃለሁ፤
 ምድሪቱን ለክፉ ሰዎች እሸጣለሁ፤
በባዕዳን እጅ፣ ምድሪቷንና በውስጧ
 ያለውን ሁሉ ባድማ አደርጋለሁ፤
እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ።
[13]“ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
“ ‘ጣዖታትን አጠፋለሁ፤
 በሜምፊስ[T] ያሉትን ምስሎች
 እደመስሳለሁ።
ከእንግዲህ በግብፅ ገዥ አይኖርም፣
 በምድሪቱም ላይ ፍርሀት እሰዳለሁ።
[14]ጳትሮስን ባድማ አደርጋለሁ፤
 በጣኔዎስ ላይ እሳት እለኵሳለሁ፤
 በቴብስ[U] ላይ ቅጣት አመጣለሁ።
[15]የግብፅ ምሽግ በሆነችው፣
 በሲን ላይ መዓቴን አፈሳለሁ፤
 ስፍር ቍጥር የሌለውን የቴብስን ሕዝብ
 አጠፋለሁ።
[16]በግብፅ ላይ እሳት እነዳለሁ፤
 ሲን በጭንቅ ትናጣለች፤
ቴብስ በማዕበል ትወሰዳለች፤
 ሜምፊስ በማያቋርጥ ጭንቀት ውስጥ
 ትገባለች።
[17]የሄልዮቱና[A] የቡባስቱ[*] ጕልማሶች፣
 በሰይፍ ይወድቃሉ፤
 ከተሞቹ ራሳቸውም ይማረካሉ።
[18]የግብፅን ቀንበር በምሰብርበት ጊዜ፣
 በጣፍናስ ቀኑ ይጨልማል፤
ከዚያም የተኵራራችበት ብርታት
 ይንኰታኰታል።
 በደመና ትሸፈናለች፤
 መንደሮቿም ይማረካሉ።
[19]ስለዚህ በግብፅ ላይ ቅጣቴን አመጣለሁ፤
 እነርሱም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ
 ያውቃሉ።’ ”

[20]በዐሥራ አንደኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ወር በሰባተኛው ቀን፣ የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [21]“የሰው ልጅ ሆይ፤ የግብፅን ንጉሥ የፈርዖንን ክንድ ሰብሬአለሁ፤ ይፈወስ ዘንድ ክንዱ አልተጠገነም፤ ወይም ሰይፍ መያዝ ይችል ዘንድ እጁ በመቃ አልታሰረም። [22]ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ በግብፅ ንጉሥ በፈርዖን ላይ ተነሥቻለሁ፤ ደኅናውንና የተሰበረውን፣ ሁለቱንም ክንዶቹን እሰብራለሁ፤ ሰይፉም ከእጁ እንዲወድቅ አደርጋለሁ። [23]ግብፃውያንን በሕዝቦች መካከል እበትና ቸዋለሁ፤ በአገሮችም መካከል እዘራቸዋለሁ። [24]የባቢሎንን ንጉሥ ክንድ አበረታለሁ፤ ሰይፌንም አስይዘዋለሁ፤ የፈርዖንን ክንድ ግን እሰብራለሁ፤ እርሱም በፊቱ ክፉኛ እንደ ቈሰለ ሰው ያቃስታል። [25]የባቢሎንን ንጉሥ ክንድ አበረታለሁ፤ የፈርዖን ክንድ ግን ይዝላል፤ ሰይፌን በባቢሎን ንጉሥ እጅ ሳስይዝ፣ እርሱም ሲነቀንቀው፣ ያኔ እኔ እግዚአብሔር መሆኔን ያውቃሉ። [26]በሕዝቦች መካከል እበትናቸዋለሁ፤ በአገሮችም መካከል እዘራቸዋለሁ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር መሆኔን ያውቃሉ።”

## የሊባኖስ ዝግባ

**31** [1]በዐሥራ አንደኛው ዓመት፣ በሦስተኛው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ለግብፅ ንጉሥ ለፈርዖንና ስፍር ቍጥር ለሌለው ሕዝቡ እንዲህ በል፤
“ ‘በክብር ከአንተ ጋር ማን ሊወዳደር
 ይችላል፤

30፥11 ቍ24-25፤ ሕዝ28፥7
30፥12 ኢሳ19፥6፤ ኤር46፥8፤ሕዝ19፥7፤ 29፥9
30፥13 ኢሳ19፥13፤ ኤር43፥12፤ሕዝ6፥6፤ ዘካ10፥11
30፥14 ዘኍ13፥22፤ ኤር46፥25፤ ሕዝ 29፥14
30፥16 ኢሳ7፥15፤ ኢሳ19፥13
30፥17 ዘፍ41፥45
30፥18 ቍ3፤ ዘሌ26፥13፤ኢሳ9፥4፤ ኤር43፥7
30፥19 ሕዝ28፥22
30፥20 ሕዝ26፥1፤ 29፥17፤31፥1፤32፥1
30፥21 ኤር30፥13፤ 44፥30፤46፥11፤ 48፥25
30፥22 ዘፍ15፥18፤ መዝ37፥17፤ ኤር46፥25፤ ዘካ11፥17
30፥23 ሕዝ29፥12
30፥24 ኤር51፥52፤ ሕዝ 21፥14፤ ሶፎ 2፥12፤ ዘካ10፥6፡12፤12፥5
30፥25 1ዜና21፥12፤ ኢሳ10፥5፤45፥1፤ ሕዝ29፥19
30፥26 ሕዝ29፥12
31፥1 ኤር52፥5፤ ሕዝ30፥20፤32፥17

[T]13 ዕብራይስጡ ኖፍ ይለዋል፤ እንዲሁም በቍ16
[U]14 ዕብራይስጡ ኖ ይለዋል፤ እንዲሁም በቍ15 እና 16
[A]17 ዕብራይስጡ አዌን (ወይም አን) ይለዋል
[*]17 ዕብራይስጡ ፊቢሴት ይላል

30፥11 *ከአሕዛብ ሁሉ እጅግ ጨካኝ የሆኑት፤* ይህ ሐረግ በጭካኔአቸው የታወቁትን ባቢሎናውያንን የሚያመለክት የተለመደ አባባል ነው (2ነገ 25፥7 ይመ)።

30፥13 *ጣዖታትን፤* የ6፥4 ማብ ይመ። *ሜምፊስ፤* ከካይሮ በስተ ደቡብ 24 ኪሎ ሜትር ያህል ርቀት ላይ የምትገኝ ስትሆን ጥንት የግብፅ ዋና ከተማና ከግብፅ ከተሞችም ሁሉ ትልቅ ነበረች። የከተሞቹ ዝርዝር መጠቀሱ የተለየ ነገር ለመግለጽ ሳይሆን፣ መጥፋታቸውን የበለጠ ለማረጋገጥ ነው (ከኢሳ10፥9-11፡27-32፤ ሚክ1፥10-15፤ ሶፎ2፥4 ጋር ያነጻጽሩ)። *ገዥ፤* ንጉሥ ነው።

30፥14 *ጳትሮስ፤* 29፥14 እና ማብ ይመ። *ጣኔዎስ፤* ራምሴ ተብላ የምትጠራው በሰሜናዊ ምሥራቅ ግብፅ የምትገኝ ከተማ ናት (ዘፀ1፥11፤ ኢሳ19፥11፡13፤ 30፥4 ይመ)። *ቴብስ፤* የጣኔዎስ ዋና ከተማ ናት።

30፥15 *ሲን፤* በምሥራቁ የዐባይ ወንዝ መፋሰሻ ላይ የምትገኝ ፔሉሲየም የምትባል የምሽግ ከተማ ናት።

30፥17 *ሄልዮቱ፤* በግሪክ “የፀሐይ ከተማ” የተባለችው የአን ከተማ ናት (አግራጌ ትርጕሙን ይመ)፤ እርስዋም ከካይሮ በስተ ሰሜን ምሥራቅ ስድስት ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ የምትገኝ ናት። *ቡባስቱ፤* ከካይሮ በስተ ሰሜን ምሥራቅ ስልሳ አራት ኪሎ ሜትር ያህል ርቀት ላይ የምትገኝ፣ በአንድ ወቅትም የታችኛው ግብፅ ዋና ከተማ ነበረች።

30፥18 *ጣፍናስ፤* በስተ ሰሜን ምሥራቅ ግብፅ ጫፍ ላይ የምትገኝ ስትሆን፣ የቃሬያ ልጅ ዮሐናንና ጭፍሮቹ ጎዶልያስ ከተገደለ በኋላ የሸሹት ወደዚች ቦታ ነበር (ኤር43፥4-7ይመ)። *ይጨልማል፤* ሞትን፣ መደምሰስንና ጥፋትን የሚገልጽ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የተለመደ ተለዋዋጭ ዘይቤ ነው። *በደመና ትሸፈናለች፤* ቍ3 እና ማብ ይመ፤ 32፥7 ይመ።

*30፥20፤* በግብፅ ላይ የተነገረ አራተኛው ንግር ነው (የ29፥1 ማብ ይመ)። *በዐሥራ አንደኛው ዓመት፣ በመጀመሪያው ወር፣ በሰባተኛው ቀን፤* ዘመኑ ሚያዝያ 29 ቀን 587 ዓ.ቅ.ክ. ሲሆን፣ ይህም በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተጠቀሰው ስምንተኛው ቀን ነው (1፥2፤ 8፥1፤ 20፥1፤ 24፥1፤ 26፥1፤ 29፥1፡17)።

30፥21 *ክንድ ሰብሬአለሁ፤ ፈርዖን ሖፍራ* ከዓመት በፊት በናቡከደነፆር መሸነፋን ያመለክታል (የ29፥6 ማብ ይመ እንዲሁም 37፥10 ይመ)።

30፥24 *ሰይፌንም አስይዘዋለሁ፤* የ21፥3 ማብ ይመ።

*31፥1፤* በግብፅ ላይ የተነገረ አምስተኛው ንግር ነው (የ29፥1 ማብ ይመ)። *በዐሥራ አንደኛው ዓመት፣ በሦስተኛው ወር በመጀመሪያው ቀን፤* ሰኔ 21 ቀን 587 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው፤ ይህ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተጠቀሰው ዘጠነኛው ቀን ነው (1፥2፤ 8፥1፤ 20፥1፤ 24፥1፤ 26፥1፤ 29፥1፡17፤ 30፥20)።

[3]ለጫካው ጥላ የሆኑ የሚያማምሩ
ቅርንጫፎች የነበሩትን፣
እጅግ መለሎ ሆኖ፣
ጫፉ ሰማይ የደረሰውን፣
የሊባኖስን ዝግባ አሦርን ተመልከት።
[4]ውሆች አበቀሉት፤
ጥልቅ ምንጮች አሳደጉት፤
ጅረቶቻቸው ፈሰሱ፤
የሥሮቹንም ዙሪያ ሁሉ አረሰረሱ፤
በመስኩ ላይ ወዳሉት ዛፎች ሁሉ፣
መስኖዎቻቸውን ለቀቁት።
[5]ስለዚህ በደን ካሉት ዛፎች ሁሉ፣
እጅግ ከፍ አለ፤
ቅርንጫፎቹ በዙ፤ ቀንበጦቹ ረዘሙ፤
ከውሃውም ብዛት የተነሣ ተስፋፉ።
[6]የሰማይ ወፎች ሁሉ፣
በቅርንጫፎቹ ላይ ጐጆአቸውን ሠሩ፤
የምድር አራዊት ሁሉ፣
ከቅርንጫፎቹ ሥር ግልገሎቻቸውን
ወለዱ።
ታላላቅ መንግሥታትም ሁሉ፣
ከጥላው ሥር ኖሩ።
[7]ከተንሰራፉት ቅርንጫፎቹ ጋር፣
ውበቱ ግሩም ነበር፤
ብዙ ውሃ ወዳለበት፣
ሥሮቹ ጠልቀው ነበርና።
[8]በእግዚአብሔር ገነት ያሉ ዝግባዎች፣
ሊወዳደሩት አልቻሉም፤
የጥድ ዛፎች፣
የእርሱን ቅርንጫፎች አይተካከሉትም፤
የአስታ ዛፎችም፣
ከእርሱ ቅርንጫፎች ጋር አይወዳደሩም፤
በእግዚአብሔር ገነት ያለ ማናቸውም ዛፍ፣
በውበት አይደርስበትም።
[9]በብዙ ቅርንጫፎች፣
ውብ አድርጌ ሠራሁት፤
በእግዚአብሔርም የአትክልት ቦታ፣
በገነት ያሉትን ዛፎች የሚያስቀና
አደረግሁት።

[10]" 'ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ጥቅጥቅ ባለው ቅጠል ላይ ጫፉን ከፍ በማድረግ ራሱን በማንጠራራቱ፣ በርዝማኔ ውም በመኵራራቱ፣ [11]እንደ ክፋቱ መጠን የሥራውን ይከፍለው ዘንድ፣ ለአሕዛብ ገዥ አሳልፌ ሰጠሁት። አውጥቼ ጥየዋለሁ፤ [12]ከአሕዛብ ወገን እጅግ ጨካኝ የሆኑትም ባዕዳን ሰዎች ቈራርጠው ጣሉት። ቀንበጦቹ በተራራዎቹና በሸለቆዎቹ ሁሉ ላይ ወድቀ ዋል፤ ቅርንጫፎቹም በውሃ መውረጃዎቹ ሁሉ ላይ ተሰባብረው ወድቀዋል፤ የምድሪቱ ሰዎች ሁሉ ከጥላው ሥር በመውጣት ትተ ውት ሄደዋል። [13]የሰማይ ወፎች ሁሉ በወደቀው ዛፍ ላይ ሰፈሩ፤ የምድር አራ ዊት ሁሉ በወደቀው ዛፍ ቅርንጫፎች ላይ ሰፈሩ። [14]ስለዚህ በውሃ አጠገብ ያለ ማንኛ ውም ዛፍ፣ ጫፎቹን ችምችም ካለው ቅጠል በላይ ከፍ በማድረግ፣ ከእንግዲህ ራሱን በትዕቢት አያንጠራራም። ከእንግዲህ ውሃ በሚገባ ያገኘ ማንኛውም ዛፍ ወደዚህ ዕይ ታቱ ከፍታ አይደርስም። ሁሉም ከምድር በታች ወደ ጕድጓድ ከሚወርድ ሟች ጋር አብሮ እንዲሞት ተወስኖበታልና።"

[15]" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ወደ መቃብር[*] በወረደበት ቀን ጥልቅ ምንጮችን ስለ እርሱ በሐዘን ሸፈንኋቸው፤ ወንዞቹን ገታሁ፤ ታላላቅ ፈሳሾችም ተቋ ረጡ። በእርሱም ምክንያት ሊባኖስን ጨለማ አለበስሁ፤ የደን ዛፎችም ሁሉ ደረቁ። [16]ወደ ጕድጓድ ከሚሄዱት ጋር ወደ መቃብር ባወረድሁት ጊዜ ሲወድቅ በተሰማው ድምፅ አሕዛብ ደነገጡ። ከዚያም የዔድን ዛፎች ሁሉ፣ ምርጥና ልዩ የሆኑት የሊባኖስ ዛፎች፣ ውሃ የጠገቡትም ዛፎች ሁሉ ከምድር በታች ሆነው ተጽናኑ። [17]ከአሕዛብ መካከል ከእርሱ ጋር ያበሩ፣ በጥላው ሥር የኖሩ፣ በሰይፍ ከሞቱት ጋር ለመቀላቀል ወደ መቃብር ወርደዋል።"

[18]" 'በዔድን ካሉት ዛፎች በውበትና በት ልቅነት የሚወዳደርህ የትኛው ነው? ይሁን እንጂ አንተም እንደዚሁ ከዔድን ዛፎች ጋር ከመሬት በታች ትወርዳለህ፤ በሰይፍ ከተገ ደሉት፣ ካልተገረዙትም መካከል ትጋደማ ለህ።

" 'እንግዲህ ፈርዖንና ስፍር ቍጥር የሌ ለው ሕዝቡ የሚደርስባቸው ይህ ነው፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።' "

31፥3 2ነገ19፥23፤ ኢሳ10፥34፤ ኤር 50፥18፤ ሕዝ19፥11፤ ዕን2፥17፤ዘካ11፥1
31፥4 ሕዝ17፥7፤ ዳን4፥10
31፥5 ቍ10፤ዘኍ 24፥6፤ሕዝ17፥5
31፥6 ዘፍ31፥7-9፤ ሕዝ17፥23፤ማቴ 13፥32
31፥7 ኢዮ14፥9
31፥8 ዘፍ2፥8-9፤ 30፥37፤መዝ80፥10
31፥9 ዘፍ2፥8፤ 13፥10፤ሕዝ28፥13
31፥10 ኢሳ2፥11፤ 14፥13-14፤ሕዝ 28፥17
31፥11 ዳን5፥20
31፥12 ሕዝ28፥7፤ 32፥5፤11-12፤35፥8፤ ዳን4፥14
31፥13 ኢሳ18፥6፤ ሕዝ29፥5፤32፥4
31፥14 ዘኍ14፥11፤ መዝ49፥14፤63፥9፤8 2፥7፤ሕዝ26፥20፤ 32፥24
31፥15 2ሳሙ1፥21
31፥16 ዘፍ2፥8፤ ኢሳ14፥8፤15፤ኤር 49፥21፤ሕዝ14፥22፤ 32፥18
31፥17 መዝ9፥17
31፥18 ኤር9፥26

[*]15 ዕብራይስጡ ሲኦል ይላል፤ እንዲሁም በቍ16 እና 17

31፥3 *አሦርን ተመልከት፤* ቀድሞ ታላቅ የነበረና በኋላ ግን የወደቀ መንግሥት ነው። በ609 ዓ.ቅ.ክ. ፈርዖን ኒካዑ በባቢሎናውያን ጥቃት እጅግ ተጨንቆ የነበረውን የአሦርን መንግሥት ለመርዳት ወደ ከርሚሽ ቢሄድም፣ ጥረቱ ስላልተሳካለት አሦር ገናና ታሪኳን አጥታለች። *ሊባኖስ፤* በዝግባ ዛፍዋ እጅግ የታወቀች አገር ነበረች (ቍ15-18፤ መሳ9፥15፤ 1ነገ4፥33፤ 5፥6፤ 2ነገ14፥9፤ ዕዝ3፥7፤ መዝ29፥5፤ 92፥12፤ 104፥16 ይመ)።

31፥4 *ውሆች፤* የኤፍራጥስንና የጤግሮስን ወንዞች ነው። *ጥልቅ ምንጮች፤* ወይም "ጥልቁ" የተባለው ነው (የ26፥19 ማብ ይመ)።

31፥6 *የሰማይ ወፎች፤* 17፥23 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዳን4፥12 ይመ።

31፥8 *በእግዚአብሔር ገነት፤* እዚህ ላይ የትዕቢት ሐሳብ ተንጸባርቆአል (ቍ10 ይመ፤ ከ28፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

31፥11 *እንደ ክፋቱ መጠን፤* ትዕቢቱን ለማመልከት ነው (ቍ10፤ ዘፍ11፥1-8 ይመ)። *ለአሕዛብ ገዥ፤* ምናልባት ናቡፖላሳር ወይም ናቡከደነፆር ነው።

31፥12 *እጅግ ጨካኝ፤* ባቢሎንን ነው (የ30፥11 ማብ ይመ)።

31፥15 *መቃብር፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። *ጥልቅ ምንጮች፤* የቍ4 ማብ ይመ።

31፥16 *አሕዛብ ደነገጡ፤* ጢሮስ በወደቀች ጊዜ ለማለት ነው (27፥35፤ 28፥19 ይመ)። *ተጽናኑ፤* ይህ የተነገረው ከኀያላን በላይ የነበሩትን ዛፎች ሁሉ በመቃብር ስላገኙአቸው ነው።

31፥17 *በሰይፍ ከሞቱት፤* ያለጊዜአቸው የተቀጠፉትን ለማመልከት ነው።

31፥18 *አንተም፤* የግብፁን ንጉሥ ፈርዖንን ነው፣ በአሦር እንደ ተደረገው ሁሉ በአንተም አይቀርልህም ማለት ነው። *ካልተገረዙት፤* የ28፥10 ማብ ይመ።

## ስለ ፈርዖን የወጣ ሙሾ

**32** በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት፣ በዐሥራ ሁለተኛው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ለግብፅ ንጉሥ ለፈርዖን ሙሾ አውርድ፤ እንዲህም በለው፤

" 'አንተ በሕዝቦች መካከል እንደ አንበሳ፣
በባሕሮችም ውስጥ እንደ አስፈሪ
አውሬ ነህ፤
በወንዞችህ የምትንቦጫረቅ፣
ውሃውን በእግርህ የምትመታ፣
ምንጮችን የምታደፈርስ ነህ::

[3]" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

" 'ብዙ ሕዝብ ይዤ፣
መረቤን በላይህ ላይ እጥላለሁ፤
በመረቤም ጎትተው ያወጡሃል::
[4]በምድር ላይ እጥልሃለሁ፤
ሜዳም ላይ እዘረጋሃለሁ፤
የሰማይ ወፎች ሁሉ እንዲሰፍሩብህ
አደርጋለሁ፤
የምድር አራዊት ሁሉ በመስገብገብ
ይበሉሃል::
[5]ሥጋህን በተራሮች ላይ እበታትነዋለሁ፤
የተረፈውንም በየሸለቆው እሞላዋለሁ::
[6]እስከ ተራሮች ባለው መንገድ ሁሉ፣
በሚፈሰው ደምህ ምድሪቱን አርሳታለሁ፤
ሸለቆዎችም በሥጋህ ይሞላሉ::
[7]አንተን በማጠፋ ጊዜ ሰማያትን
እሸፍናለሁ፤
ከዋክብታቸውንም አጨልማለሁ፤
ፀሓይን በደመና እሸፍናለሁ፤
ጨረቃም ብርሃኗን አትሰጥም::
[8]በሰማይ የሚያበሩትን ብርሃናት ሁሉ፣
በአንተ ላይ አጨልማለሁ፤
በምድርህ ላይ ጨለማን አመጣለሁ፤
ይላል ጌታ እግዚአብሔር::
[9]በማታውቀው ምድር፣
በሕዝቦች መካከል ያንተን ጥፋት
ሳመጣ፣ሣ
የብዙ ሕዝብን ልብ አስጨንቃለሁ::
[10]ሕዝቦች በአንተ ላይ ከደረሰው የተነሣ
እንዲደነግጡ አደርጋለሁ፤
ሰይፌን በፊታቸው ስነቀንቅ፣
በአንተ ላይ ከደረሰው ሁኔታ የተነሣ
ንጉሦቻቸው ይንቀጠቀጣሉ::
አንተ በምትወድቅበት ቀን፣
እያንዳንዳቸው ስለ ራሳቸው ሕይወት
በመፍራት፣
በየቅጽበቱ ይርበደበዳሉ::
[11]" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላልና፤

" 'የባቢሎን ንጉሥ ሰይፍ፣
በአንተ ላይ ይመጣል::
[12]ከሕዝቦች ሁሉ እጅግ ጨካኝ በሆኑት፣
በኀያላን ሰዎች ሰይፍ፣
ያከማቸኸው ሰራዊት እንዲወድቅ
አደርጋለሁ፤
የግብፅን ኵራት ያንኰታኵታሉ፤
የሰራዊቷም ብዛት ይጠፋል፤
[13]ብዙ ውሃ ባለበት አጠገብ ያለውን፣
የከብት መንጋዋን አጠፋለሁ፤
ከእንግዲህ የሰው እግር አይረጋግጠውም፤
የከብትም ኰቴ አያደፈርሰውም::
[14]ከዚያም ውሆቿን አጠራለሁ፤
ወንዞቿም እንደ ዘይት እንዲፈሱ
አደርጋለሁ፤
ይላል ጌታ እግዚአብሔር::
[15]ግብፅን ባድማ ሳደርጋት፣
ምድሪቱም ያላትን ሁሉ ያጣች ስትሆን፣
በዚያም የሚኖሩትን ሁሉ ስመታ፣
ያን ጊዜ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ
ያውቃሉ::"

[16]"ስለ እርሷ የሚያወርዱት ሙሾ ይህ ነው፤ የሕዝቦች ሴት ልጆች ያዜሙታል፤ ስለ ግብፅና ስለ ብዙ ሰራዊቷ ሁሉ ሙሾ ያወርዳሉ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር::"

32፥1 ሕዝ31፥1፤ 33፥21
32፥2 ቍ13፤ ዘፍ1፥21፤ 2ሳሙ1፥17፤ 2ነገ24፥1፤ 2ዜና35፥25፤ ኢዮ3፥8፤41፥31፤ መዝ74፥13፤ሕዝ19፥1፤ 29፥3፤34፥18፤ ናሆ2፥11-13
32፥3 ሕዝ12፥13፤ ዕን1፥15
32፥4 ኢሳ18፥6፤ ሕዝ31፥12-13፤ 39፥4-5፡17
32፥5 ሕዝ31፥12
32፥6 ኢሳ34፥3፤ ሕዝ29፥5
32፥7 ኢሳ13፥10፤ 34፥4፤ሕዝ30፥3፤ ኢዩ2፥2፡31፤3፥15፤ ማቴ24፥29፤ ራእ8፥12
32፥8 ኢዮ9፥7፤ መዝ 102፥26፤ ኤር4፥23፤ኢዩ2፥10
32፥10 ኢሳ30፥32፤ ኤር46፥10፤ ሕዝ26፥16፤27፥35፤ 30፥9፤ራእ18፥9-10
32፥11 ኢሳ19፥4፤ ኤር46፥13፤ ሕዝ21፥19፤29፥19
32፥12 ሕዝ28፥7፤ 31፥11-12
32፥13 ቍ2፤ ሕዝ29፥8፡11
32፥15 ዘፀ7፥5፤ 14፥4፡18፤ መዝ107፥33-34
32፥16 ዘፍ50፥10፤ ሕዝ19፥1

ሣ9 በዕብራይስጡም እንዲሁ ሲሆን ሰብዓ ሊቃናት ግን *በአሕዛብ መካከል ወደ ምርኮ ሳመጣው* ይላል

*32፥1፤* በግብፅ ላይ የተነገረ ስድስተኛው ንግር ነው (የ29፥1 ማብ ይመ):: *በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት፣ በዐሥራ ሁለተኛው ወር በመጀመሪያው ቀን፤* መጋቢት 3 ቀን 585 ዓ.ቅ.ክ. ማለት ነው፤ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተጠቀሰው ዐሥረኛው ቀን ነው (1፥2፤ 8፥1፤ 20፥1፤ 24፥1፤ 26፥1፤ 29፥1፡17፤ 30፥20፤ 31፥1):: የሰብዓ ሊቃናትንና የሱርስቱን ትርጕም የምንከተል ከሆኑ (ዐሥራ አንደኛው ዓመት)፣ በግብፅ ላይ የተነገሩት ንግሮች በቅደም ተከተላቸው መሠረት ተቀምጠዋል፤ እንዲህ ከሆነ ደግሞ ቀኑ መጋቢት 13/586 ዓ.ቅ.ክ. ነው:: ከ29፥1፤ 30፥20፤ 31፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ ቍ17 እና ማብ ይመ::

32፥2 *ሙሾ፤* የ19፥1 ማብ ይመ:: *በሕዝቦች መካከል እንደ አንበሳ፤* ንጉሣዊነትንና ግርማ ሞገስን የሚገልጽ አባባል ነው (19፥1-9 ይመ):: *አውሬ፤* 29፥3 እና ማብ ይመ:: *ውሃውን ... ምንጮችን፤* የዐባይን ወንዝ መስኖዎች ነው (የ29፥3 ማብ ይመ)::

32፥3 *መረቤን ... እጥላለሁ፤* ቀደም ሲል የእግዚአብሔር መረብ የተጣለበት ሴዴቅያስ ነበር (12፥13፤ 17፥20፤ 19፥8 ይመ)::

32፥4 *እጥልሃለሁ፤* እዚህ ላይ ከተገለጸው የእግዚአብሔር ድርጊት በ29፥3-5 ከተጠቀሰው ጋር ተመሳሳይ ነው::

32፥7 *ሰማያትን እሸፍናለሁ፤* የእግዚአብሔርን ቀን ከጨለማ ጋር በማያያዝ ከተጠቀሱት ሰባት አስፈሪ ሐረጎች አንዱ ነው (ኢዩ2፥2፡10፡31፤ 3፥15፤ አሞ5፥18-20፤ ሶፎ1፥15 ይመ)::

32፥9 *ልብ አስጨንቃለሁ፤* ይህና የሚቀጥለው ቍጥር በዓለም የተነሡ ኀያላን መንግሥታት በወደቍ ቍጥር የሚከሠተውን ታላቅ ፍርሀት የሚያመለክትና ታናናሽ መንግሥታትም ይበልጥ ጕዳት ሊደርስባቸው እንደሚችል ያሳያል፤ ይህን ጢሮስ ስትወድቅ ከተፈጠረው ተመሳሳይ ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ (26፥16-18፤ 27፥35፤ 28፥19)::

32፥10 *ሰይፌን፤* የ21፥3 ማብ ይመ::

32፥11 *የባቢሎን ንጉሥ፤* ናቡከደነፆርን ነው (ከ21፥19 ጋር ያነጻጽሩ)::

32፥12 *ከሕዝቦች ሁሉ እጅግ ጨካኝ፤* የባቢሎንን መንግሥት ማለት ነው (የ30፥11 ማብ ይመ)::

32፥14 *ወንዞቿም እንደ ዘይት እንዲፈሱ፤* ሕይወት ያለው ማንኛውም ነገር የውሃውን ወለል ምንም ሊያደርስበት አይችልም፤ እንዲህ ዐይነቱ ሥጋት ውስጥ የሚጥል አባባል በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በተለዋጭ ዘይቤነት የተጠቀሰው እዚህ ላይ ብቻ ነው::

32፥16 *የሕዝቦች ሴት ልጆች፤* ሙሾ የሚያወርዱ ታዋቂ ሴቶች ናቸው (ኤር9፥17-18 ይመ)::

[17]በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት፣ ከወሩም በዐሥራ አምስተኛው ቀን የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [18]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ስለ ብዙው የግብፅ ሰራዊት አልቅስ፤ እርሷንና የኀያላንን ሕዝቦች ሴት ልጆች ወደ ጕድጓድ ከሚወርዱት ጋር ከምድር በታች አውርዳቸው:: [19]እንዲህም በላቸው፤ ‘እናንተ ከሌሎች የተለያችሁ ናችሁን? ውረዱ፤ ባልተገረዙትም መካከል ተጋደሙ::’ [20]እነርሱም በሰይፍ በተገደሉት መካከል ይወድቃሉ፤ ሰይፉ ተመዟል፤ ከብዙ ሰራዊቷ ሁሉ ጋር ትጐተት:: [21]በመቃብርም[ሀ] ውስጥ ኀያላኑ መሪዎች ስለ ግብፅና ስለ ተባባሪዎቿ፣ ‘ወደ ታች ወርደዋል፤ በሰይፍ ከተገደሉትና ካልተገረዙትም ጋር በአንድ ላይ ተጋድመዋል’ ይላሉ::

[22]“አሦር ከመላው ሰራዊቷ ጋር በዚያ ትገኛለች፤ በሰይፍ በወደቁባትና በታረዱባት ሰዎች ሁሉ መቃብር ተከባለች:: [23]መቃብራቸው በጥልቁ ጕድጓድ ውስጥ ነው፤ ሰራዊቷም በመቃብሯ ዙሪያ ተረፍርፏል:: በሕያዋን ምድር ሽብርን የነዙ ሁሉ ታርደዋል፤ በሰይፍም ወድቀዋል::

[24]“ኤላም በዚያ አለች፤ ሰራዊቷም ሁሉ በመቃብሯ ዙሪያ አለ፤ ሁሉም ታርደዋል፤ በሰይፍ ወድቀዋል:: በሕያዋን ምድር ሽብር የነዙ ሁሉ ሳይገረዙ ከምድር በታች ወርደዋል፤ ወደ ጕድጓድ ከወረዱት ጋር ዕፍረታቸውን ተሸክመዋል፤ [25]በመቃብሯ ዙሪያ ካለው መላው ሰራዊቷ ጋር፣ በታረዱት መካከል መኝታ ተዘጋጅቶላታል:: ሁሉም ያልተገረዙና በሰይፍ የተገደሉ ናቸው፤ ሽብራቸው በሕያዋን ምድር ስለ ተነዛ፣ ወደ ጕድጓድ ከሚወርዱት ጋር ዕፍረታቸውን ይሸከማሉ፤ በታረዱትም መካከል ይጋደማሉ::

[26]“ሞሳህና ቶቤል መቃብሮቻቸው በብዙ ሰራዊታቸው መቃብር ተከበው ይገኛሉ፤ ሁሉም ያልተገረዙ ሲሆኑ፣ በሕያዋን ምድር ሽብራቸውን ስለ ነዙ በሰይፍ ተገድለዋል:: [27]ከዘመናት በፊት ከወደቁት ከኀያላን ሰዎች፣ ከእነዚያ ሰይፋቸውን ተንተርሰው፣ ጋሻቸውንም ደረታቸው ላይ ይዘው ከነሙሉ ትጥቃቸው ወደ መቃብር ከወረዱት ጋር አይጋደሙምን? የእነዚህ ተዋጊዎች ሽብር በሕያዋን ምድር ባሉት ኀያላን ላይ ቢደርስም የኀጢአታቸው ቅጣት በዐጥንታቸው ላይ ይሆናል::

[28]“ፈርዖን ሆይ፤ አንተም እንደዚሁ ትሰበራለህ፤ በሰይፍ ከተገደሉት ከእነዚያ ካልተገረዙት ጋር ትጋደማለህ::

[29]“ኤዶምም በዚያ አለች፤ ንጉሦቿና ገዦቿም ሁሉ በዚያ አሉ፤ ኀይል የነበራቸው ቢሆኑም፣ በሰይፍ ከተገደሉት ጋር ተጋድመዋል፤ ወደ ጕድጓድ ከወረዱት፣ ከእነዚያ ካልተገረዙትም ጋር ተኝተዋል::

[30]“የሰሜን ገዦች በሙሉ፣ ሲዶናውያንም ሁሉ በዚያ ይገኛሉ፤ ከዚህ በፊት በኀይላቸው ምክንያት ሽብር የፈጠሩ ቢሆኑም፣ ከታረዱት ጋር በኀፍረት ወረዱ፤ ሳይገረዙም በሰይፍ ከተገደሉት ጋር ይጋደማሉ፤ ወደ ጕድጓድ ከወረዱትም ጋር ኀፍረታቸውን ይሸከማሉ::

[31]“ፈርዖንና ሰራዊቱ ሁሉ ያዩአቸዋል፤ በሰይፍ ከተገደለበት ሰራዊትም ሁሉ ሐዘን ይጽናናል፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር:: [32]በሕያዋን ምድር ሽብር እንዲያስፋፋ ብፈቅድም እንኳ፣ ፈርዖንና ሰራዊቱ ሁሉ በሰይፍ ከተገደሉት ጋር ባልተገረዙት መካከል ይጋደማሉ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር::

## ሕዝቅኤል ጕበኛው

**33** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ለአገርህ ሰዎች ተናገር፤ እንዲህም በላቸው፤ ‘በምድር ላይ ሰይፍን ሳመጣ፣ የምድሪቱ ሕዝብ ከሰዎቻቸው አንዱን መርጠው ጕበኛ ቢያደርጉት፣ [3]እርሱም በምድሪቷ ላይ ሰይፍ ሲመጣ አይቶ፣ ሕዝቡን ለማስጠንቀቅ መለከት ቢነፋ፣ [4]ከዚያም ማንም መለከቱን ሰምቶ ባይጠነቀቅ፣ ሰይፍም መጥቶ ሕይወቱን ቢያጠፋ፣ ደሙ በገዛ ራሱ ላይ ይሆናል:: [5]የመለከቱን ድምፅ ሰምቶ ባለመጠንቀቁ፣ ደሙ በገዛ ራሱ ላይ ይሆናል፤ ቢጠነቀቅ ኖሮ

[ሀ]21 ዕብራይስጡ ሲኦል ይላል፤ በቍ 27ትም እንዲሁ

32+17 ቍ1
32+18 ኤር1+10፤ ሕዝ26+20፤31+14፡16፤ሚክ1+8
32+19 ቍ29-30፤ ሕዝ28+10
32+20 መዝ28+3፤ ሕዝ31+17-18
32+21 ኢሳ14+9፤ ሕዝ28+10
32+23 ኢሳ14+15፤ ናሆ1+14
32+24 ዘፍ10+22፤ ኢዮ28+13፤ኤር 49+37፤ሕዝ26+20
32+25 ሕዝ28+10
32+26 ሕዝ27+13
32+27 ሕዝ28+10
32+29 መዝ137+7፤ ኢሳ34+5-15፤ኤር 49+7፤ሕዝ25+12 -14፤35+15፤አብ1+1
32+30 ዘፍ10+15፤ ኢሳ14+31፤ ኤር25+22፡26፤ ሕዝ26+20፤28+8፡10፤38+6፤ 39+2
32+31 ሕዝ14+22
32+32 ኢዮ3+14፤ ኤር44+30
33+3 ዘፀ20+18፤ ዘኍ10+7፤ሆሴ5+8፤ 8+1
33+4 ዘሌ20+9፤ 2ዜና25+16፤ኤር6+17፤ዘካ1+4፤ሐሥ18+6
33+5 ዘፀ9+21፤ ዘሌ20+9

*32+17፤* ይህ በግብፅ ላይ የተነገረው ሰባተኛውና የመጨረሻው ንግር ነው (የ29+1 ማብ ይመ):: *በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት ... በዐሥራ አምስተኛው ቀን፤* ስንተኛው ወር እንደ ሆነ አልተገለጸም (ከ26+1፤ 40+1 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ሆኖም የተጠቀሰው ዓመት ከሚያዝያ 13 ቀን 586 እስከ ሚያዝያ 1 ቀን 585 ዓ.ቅ.ክ. ድረስ ያለውን ጊዜ በሙሉ ያካትታል:: የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም እንደሚለው ከሆነ፣ የመጀመሪያው ወር ዐሥራ አምስተኛው ቀን፣ ሚያዝያ 27 ቀን 586 ዓ.ቅ.ክ. ይሆናል::

32+18 *ከምድር በታች፤* በ31+15 ላይ እንደ ተጠቀሰው “መቃብር” (ሲኦል) ማለት ነው:: *የኀያላን ሕዝቦች ሴት ልጆች፤* የቍ16 ማብ ይመ::

32+19 *ባልተገረዙትም፤* የ28+10 ማብ ይመ::

32+24 *ኤላም፤* ከአሦር በስተ ምሥራቅ የምትገኝ አገር ስትሆን፣ እርሷም የዛሬዪቱ ኢራን ናት::

32+26 *ሞሳህና ቶቤል፤* በትንሿ እስያ ውስጥ የሚገኙ ሕዝቦችና አገሮች ናቸው::

32+30 *ሲዶናውያን፤* የ28+21 ማብ ይመ::

*33+1-48+35፤* እስራኤል እንድትጽናና የተነገረ ክፍል ነው::

*33+1-37+28፤* ኢየሩሳሌም ከወደቀች በኋላ የተነገሩ፣ የሚያጽናኑ መልእክቶችና ንግሮች ናቸው፤ የፍርድና የማስጠንቀቂያ ቃላት ዐልፎ ዐልፎ ይገኛሉ (ለምሳሌ 33+23-29፤ 34+1-19፤ 35፤ 36+1-7)፤ ከእነዚህ አንዳንዶቹ መንፈሱ እጅግ ዝቅ ያለውን ሕዝብ ለማጽናናት የተነገሩ ናቸው::

33+2 *ለአገርህ ሰዎች፤* ከነቢዩ ከሕዝቅኤል ጋር ተማርከው የነበሩት እስራኤላውያን ናቸው:: *ሰይፍ፤* ወራሪውን ሰራዊት ነው:: *የምድሪቱ ሕዝብ፤* የራሳቸው መሬት ኖሮአቸው፣ በሰራዊቱ ውስጥ ያገለገሉና የዜግነት ሙሉ መብት ያላቸውን ነው (7+27፤ 12+19፤ 45+16፡22፤ 46+3 ይመ):: *ጕበኛ፤* ይህ ሐረግ በም3 ላይ ከተነገረ በኋላ በም18 ላይም እንዲሁ ተብራርቷል (የ3+16 ማብ ይመ)::

33+3 *መለከት፤* ከአውራ በግ ቀንድ የሚሠራ (ኢሱ 6+4፡6፡13)፣ በአደጋ ጊዜም ለማስጠንቀቂያ (ነህ4+18-20፤ ኤር 4+19፤ አሞ3+6)፤ መንፈሳዊ በዓላትን መጀመሩን ለማብሰር (ለምሳሌ የስርየት ቀን ዘሌ25+9፤ የወሩን መግቢያ መዝ81+3) የሚያገለግል የድምፅ መሣሪያ ነው::

33+4 *ደሙ በገዛ ራሱ ላይ ይሆናል፤* የ18+13 ማብ ይመ::

ግን ራሱን ባዳነ ነበር። [6]ነገር ግን ጒበኛ ሰይፍ ሲመጣ አይቶ፣ ሕዝቡን ለማስጠንቀቅ መለከት ሳይነፋ ቢቀርና ከመካከላቸው የአንዱን ሰው ሕይወት ሰይፍ ቢያጠፋ፣ ያ ሰው ስለ ኀጢአቱ ይወሰዳል፤ ጒበኛውን ግን ስለ ሰውዬው ደም ተጠያቂ አደርገዋለሁ።’

[7]“የሰው ልጅ ሆይ፤ አንተን ለእስራኤል ቤት ጒበኛ አድርጌሃለሁ፤ ስለዚህ የምናገረውን ቃል ስማ፤ ማስጠንቀቂያዬንም ስጣቸው። [8]ክፉውን፣ ‘አንተ ክፉ ሰው፤ በእርግጥ ትሞታለህ’ ባልሁት ጊዜ፣ እርሱን ከመንገዱ እንዲመለስ ባታደርገው፣ ያ ክፉ ሰው በኀጢአቱ ይሞታል፤ አንተ ግን ስለ ደሙ ተጠያቂ ትሆናለህ። [9]ነገር ግን ክፉውን ሰው ከመንገዱ እንዲመለስ ነግረኸው እሺ ባይል፣ እርሱ ስለ ኀጢአቱ ይሞታል፤ አንተ ግን ራስህን አድነሃል።

[10]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ለእስራኤል ቤት እንዲህ በል፤ ‘እንዲህ ትላላችሁ፤ “በደላችንና ኀጢአታችን ከብዶናል፤ ከዚህም[a] የተነሣ ልንጠፋ ነው፤ ታዲያ እንዴት መኖር እንችላለን?” [11]እንዲህ በላቸው፤ ‘በሕያውነቴ እምላለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ ከመንገዳቸው ተመልሰው በሕይወት እንዲኖሩ እንጂ በክፉዎች ሞት ደስ አልሰኝም። ተመለሱ! ከክፉ መንገዳችሁ ተመለሱ! የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ለምን ትሞታላችሁ?’

[12]“አሁንም የሰው ልጅ ሆይ፤ ለአገርህ ሰዎች እንዲህ በላቸው፤ ‘ጻድቅ ሰው ትእዛዝን በተላለፈ ጊዜ የቀድሞ ጽድቁ አያድነውም፤ ኀጢአተኛ ሰው ከኀጢአቱ ከተመለሰ፣ ከቀድሞ ክፋቱ የተነሣ አይጠፋም። ጻድቅ ሰው ኀጢአት ቢሠራ፣ በቀድሞ ጽድቁ ምክንያት በሕይወት እንዲኖር አይደረግም።’ [13]ጻድቁን ሰው በእርግጥ በሕይወት ትኖራለህ ብለው፣ እርሱም ጽድቁን ተማምኖ ክፋት ቢሠራ፣ ከጽድቅ ሥራው አንዱም አይታሰብለትም፤ በኀጢአቱም ምክንያት ይሞታል። [14]እንዲሁም ክፉውን ሰው፣ ‘በእርግጥ ትሞታለህ’ ብለው፣ እርሱም ከኀጢአቱ ተመልሶ ቀና የሆነውንና ትክክለኛውንም ነገር ቢያደርግ፣ [15]ለሰጠው ብድር የተቀበለውን መያዣ ቢመልስ፣ የሰረቀውንም መልሶ ቢሰጥ፣ ሕይወት የሚሰጡትን ትእዛዛት ቢከተል፣ ክፉ ነገርንም ባያደርግ፣ በእርግጥ እርሱ በሕይወት ይኖራል፤ አይሞትምም። [16]ከሠራው ኀጢአት አንዱም አይታሰብበትም፤ ቀናውንና ትክክለኛውን አድርጓልና፤ በእርግጥ በሕይወት ይኖራል።

[17]“ይህም ሆኖ የአገርህ ሰዎች፣ ‘የጌታ መንገድ ቀና አይደለችም’ ይላሉ፤ ቀና ያልሆነው ግን የእነርሱ መንገድ ነው። [18]ጻድቅ ሰው የጽድቁን ሥራ ትቶ ክፉ ነገር ቢያደርግ፣ ስለ ኀጢአቱ ይሞታል። [19]ክፉም ሰው ከክፉ ሥራው ተመልሶ ቀናውንና ትክክለኛውን ነገር ቢያደርግ፣ ይህን በማድረጉ በሕይወት ይኖራል። [20]ይሁን እንጂ የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ‘የጌታ መንገድ ቀና አይደለችም’ ትላላችሁ፤ ነገር ግን በእያንዳንዳችሁ ላይ እንደ መንገዳችሁ እፈርድባችኋለሁ።”

## የኢየሩሳሌም መውደቅ

[21]በተማረክን በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት፣ በዐሥረኛው ወር፣ በአምስተኛው ቀን፣ ከኢየሩሳሌም ያመለጠ አንድ ሰው ወደ እኔ መጥቶ፣ “ከተማዪቱ ወደቀች!” አለኝ። [22]ሰውየው ከመድረሱ በፊት በነበረው ምሽት፣ የእግዚአብሔር እጅ በላዬ ላይ ነበረች፤ በማለዳም ሰውየው ወደ እኔ ከመምጣቱ በፊት እግዚአብሔር አፌን ከፈተ፤ አፌም ተከፈተ፤ ከዚያ በኋላ ዝም አላልሁም።

[23]ከዚያም የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [24]“የሰው ልጅ ሆይ፤ በእስራኤል ምድር በፍርስራሾች ውስጥ የሚኖሩት ሕዝቦች፣ ‘አብርሃም አንድ ራሱን

33፥6 ኢሳ56፥10-11፤ሕዝ3፥18
33፥7 ኢሳ52፥8፤ ኤር1፥17፤26፥2
33፥8 ቍ14፤ ኢሳ3፥11፤ሕዝ18፥4
33፥9 መዝ7፥12፤ ሕዝ3፥17-19
33፥10 ዘሌ26፥16፤39፤ሕዝ4፥17
33፥11 2ዜና30፥9፤ ኢሳ19፥22፤ኤር3፥12፤44፥7-8፤ሰቆ3፥33፤ ሕዝ18፥23፤ሆሴ11፥8፤ኢዩ2፥12፤1ጢሞ2፥4
33፥12 ቍ2፤2ዜና7፥14፤ሕዝ3፥20፤ 18፥21
33፥13 ዕብ10፥38፤ 2ጴጥ2፥20-21
33፥14 ኤር22፥3
33፥15 ዘፀ22፥1-4፤ 26፤ዘሌ6፥2-5፤ኢሳ55፥7፤ኤር18፥7-8፤ ሉቃ19፥8
33፥16 ኢሳ43፥25፤ ኤር50፥20
33፥18 ኤር18፥10፤ ሕዝ3፥20
33፥19 ቍ14-15
33፥20 ኢዮ34፥11
33፥21 2ነገ25፥4፤ 10፤ኤር39፥1-2፤52፥4-7፤ሕዝ24፥26፤ 32፥1
33፥22 ሕዝ1፥3፤ 3፥26-27፤24፥27፤ 29፥21፤ሉቃ1፥64
33፥24 ዘዳ1፥10፤ኢሳ51፥2፤ ኤር40፥7፤ሕዝ11፥15፤36፥4፤ሉቃ3፥8፤ ሐዋ7፥5

[a]10 ወይም *በእርሱ*

33፥6 *ደም፤* ሕይወቱን ማለት ነው (ዘፍ9፥5፤ 42፥22 ይመ)።

33፥7 *የእስራኤል ቤት፤* ሕዝቡንና እያንዳንዱንም ሰው ማለት ነው፤ ከቍ7-9 ያለውን ከ3፥17-19 ጋር ያነጻጽሩ።

33፥10 *በደላችንና ኀጢአታችን፤* በምርኮ ያለው ሕዝብ፣ ኀጢአተኛ ለመጀመሪያ ተገነዘበ፤ ቀደም ብሎ ግን ይወቅሱ የነበረው አባቶቻቸውን (18፥2)፣ ይልቁንም እግዚአብሔርን ነበር (18፥19፡25)።

33፥11 *እኔ ሕያው እግዚአብሔርን፤* የ18፥3 ማብ ይመ። *ደስ አልሰኝም፤* በ18፥23 ላይ በጥያቄ መልክ ቀርቦ ነበር። በመሠረቱ እግዚአብሔር ለፍጥረቱ ያለው ዐላማ፣ ፍጥረት በሕይወት እንዲኖር እንጂ እንዲሞት አልነበረም (የ16፥6፤ ማብ ይመ)። *ተመለሱ!፤* ለሦስተኛ ጊዜ የቀረበ የንስሓ ጥሪ ነው (14፥6፤ 18፥30 ይመ)።

*33፥12-20፤* በ18፥21-29 ላይ ከተገለጸው ሐሳብ ጋር ተመሳሳይ ነው፤ ጻድቅም ሆነ ኀጢአተኛ እያንዳንዱ ሰው በየዕለቱ በጽድቅ የመኖር ምርጫ ማድረግ እንደሚገባው የሚያመለክት ነው።

33፥15 *ለሰጠው ብድር የተቀበለውን መያዣ ቢመልስ፣ የሰረቀውንም መልሶ ቢሰጥ፤* የ18፥7 ማብ ይመ። *ሕይወት የሚሰጡትን ትእዛዛት፤* እግዚአብሔር ሕግን የሰጠበት ምክንያት ሕይወትን ለማለምለምና ለመጠበቅ ነው (ከ20፥13፡21 ጋር ያነጻጽሩ)። *በእርግጥ እርሱ በሕይወት ይኖራል፤* ይህ ክፍል፣ በቍ 10 ላይ ለተጠቀሰው ጥያቄ ከሕዝቅኤል የተሰጠውን መልስ የያዘ ነው።

33፥17 *የጌታ መንገድ ቀና አይደለችም፤* ከ18፥25፡29 ጋር ያነጻጽሩ።

33፥21 *በዐሥራ ሁለተኛው ዓመት፣ በዐሥረኛው ወር፣ በአምስተኛው ቀን፤* ጥር 8 ቀን 585 ዓ.ቅ.ክ. ሲሆን፣ ይህም በኢየሩሳሌም ያለው ቤተ መቅደስ ከተቃጠለ በኋላ በአምስተኛው ወር ማለት ነው። ይህን በተመለከተ 2ነገ25፥8 ይመ፤ በዚህ ላይ የተጠቀሰው ቀን ዓ.ቅ.ክ. ነሐሴ 14/586 ነው። በኢየሩሳሌምና በባቢሎን መካከል የሚደረግ ጕዞ አራት ወር ያህል ይወስዳል (ዕዝ7፥9)። *ያመለጠ አንድ ሰው፤* በ586 ዓ.ቅ.ክ. ተማርከው ከሄዱት ከመጀመሪያዎቹ ምርኮኞች መካከል ማለት ነው (24፥26 ይመ)። *ከተማዪቱ ወደቀች፤* ሕዝቅኤል አስቀድሞ የተናገረው ትንቢት ሁሉ ተፈጽሞአል፤ እውነተኛነቱም ተረጋግጦአል። ከዚህም በመቀጠል ለሕዝቅኤል አዲስ ተልእኮ ተሰጥቶታል፤ ይኸውም በመጋቢነት ሕዝቡን ማጽናናት ነው።

33፥22 *ከዚያ በኋላ ዝም አላልሁም፤* ሕዝቅኤል አገልግሎቱን ሲጀምር እንደ ድዳ ሆኖ ነበር፤ ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ግን መናገር ጀመረ (3፥26 እና ማብ ይመ)።

33፥24 *በፍርስራሾች ውስጥ የሚኖሩት ሕዝቦች፤* በ586 ዓ.ቅ.ክ. ላይ ተማርከው ወደ ባቢሎን ያልሄዱትን የኢየሩሳሌምን

ብቻ ነበር፤ ያም ሆኖ ምድሪቱን ወረሰ፤ እኛ ግን ብዙዎች ነን፤ በእርግጥ ምድሪቱ ርስት ሆና ተሰጥታናለች’ ይላሉ:: [25]ስለዚህ እንዲህ በላቸው፣ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ሥጋውን ከነደሙ ትበላላችሁ፤ ዐይኖቻች ሁንም ወደ ጣዖቶቻችሁ ታነሣላችሁ፤ ደምም ታፈሳላችሁ፤ ታዲያ በዚህ ሁኔታ ምድሪቱን ልትወርሱ ታስባላችሁ? [26]በሰይፋችሁ ትመ ካላችሁ፤ አስጸያፊ ነገሮችን ትፈጽማላችሁ፤ እያንዳንዳችሁም የባልንጀራችሁን ሚስት ታረክሳላችሁ፤ ታዲያ በዚህ ሁኔታ ምድሪቱን ልትወርሱ ይገባችኋል?’

[27]“እንዲህ በላቸው፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በሕያውነቴ እምላለሁ፤ በፍር ስራሾች ውስጥ የተረፉት በሰይፍ ይወድቃሉ፤ በገጠር ያሉትን በጫጭቀው እንዲበሏቸው ለዱር አራዊት እሰጣቸዋለሁ፤ በምሽግና በዋሻ ያሉትም በቸነፈር ይሞታሉ:: [28]ምድ ሪቱን ጠፍና ባድማ አደርጋታለሁ፤ የምት መካበት ጕልበቷ እንዳልነበረ ይሆናል፤ የእስ ራኤልም ተራሮች ማንም እንዳያልፍባቸው ባድማ ይሆናሉ:: [29]ካደረጓቸው አስጸያፊ ነገሮች ሁሉ የተነሣ፣ ምድሪቱን ባድማ በማ ደርግበት ጊዜ፣ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::’

[30]“አንተን በሚመለከት፣ የሰው ልጅ ሆይ፤ የአገርህ ሰዎች በየቤቱ በርና ግድግዳ ሥር ሆነው ስለ አንተ ይነጋገራሉ፤ እርስ በራ ሳቸውም እንዲህ ይባባላሉ፤ ‘ኑና *ከእግዚ አብሔር* የመጣውን መልእክት እንስማ::’ [31]ሁልጊዜ እንደሚያደርጉት ሕዝቤ ወደ አንተ ይመጣሉ፤ ቃልህንም ለመስማት ከፊትህ ይቀመጣሉ፤ ነገር ግን አይፈጽሙትም:: በከ ንፈራቸው ብዙ ፍቅርን ይገልጣሉ፤ ልባቸው ያረፈው ግን ተገቢ ባልሆነ ጥቅም ላይ ነው:: [32]ቃልህን ሰምተው ሥራ ላይ የማያ ውሉት በመሆናቸው፣ አንተ ለእነርሱ ባማረ ድምፅ የፍቅር ዘፈን የሚዘፍን፣ በዜ ሪያም አሳምሮ የሚጫወት ሙዚቀኛ ሳቸዋል::

[33]“ይህ ሁሉ ሲሆን፣ በእርግጥም ይሆናል፤ በመካከላቸው ነቢይ እንደ ነበረ፣ እንዳለ ያውቃሉ::”

33+25 ዘፍ9+41 ኤር7+9-10:211 ሕዝ22+6:27
33+26 ኤር41+71 ሕዝ22+11
33+27 1ሳሙ13+ 61ኢሳ2+191 ኤር42+221 ሕዝ7+151 14+21139+4
33+28 ዘፍ6+71 ኢሳ41+151ኤር9+10
33+29 ዘሌ26+341 ኤር18+16144+221 ሕዝ36+41 ሚክ7+13
33+31 መዝ78+36 -371119+361 ኢሳ29+13133+151 ኤር3+1016+171 ሕዝ8+1122+271 ማቴ13+2211ዮሐ3+18
33+32 1ነገ4+321 ማር6+20
33+33 1ሳሙ3+ 201ኤር28+91 ሕዝ2+5
34+2 መዝ78+70 -721ኢሳ40+111 ኤር3+15123+11 ሚክ3+111ዮሐ10+1 1121+15-171 ይሁ1+12
34+3 ኢሳ56+111 ሕዝ22+271አሞ6+41 ዘካ11+5
34+4 ቍ161 ዘሌ25+431ኢሳ1+61 3+71ሚክ3+31 ዘካ11+15-17
34+5 ቍ28ዘኍ 27+171ኢሳ56+91 ሐሥ20+29
34+6 ዘሌ26+331 2ዜና18+161 መዝ95+101142+41 ኤር 10+21150+61 ሆሴ7+131ማቴ9+361 18+12-131 ሉቃ15+511ጴጥ2+25
34+8 መሳ2+141 ኢሳ56+91ይሁ1+12

## እረኞችና በጎች

**34** *የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]“የሰው ልጅ ሆይ፤ በእስራኤል እረኞች ላይ ትንቢት ተናገር፤ ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በላቸው፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ራሳቸውን ብቻ ለሚንከባከቡ ለእስራኤል እረኞች ወዮላቸው! እረኞች መንጋውን ማሰማራት አልነበረባቸውምን? [3]ሙማውን ትበላላችሁ፤ ከጠጕሩ የተሠራውን ሱፍ ትለብሳላችሁ፤ የሰባውን ዐረዳችሁ፤ ነገር ግን መንጋውን አትንከባከቡትም:: [4]ደካማውን አላበረታችሁ ትም፤ በሽተኛውን አልፈወሳችሁትም፤ የተ ጐዳውንም አልጠገናችሁትም:: የባዘኑትን አልመለሳችሁም፤ የጠፉትንም አልፈለጋች ሁም፤ በግፍና በጭካኔ ገዛችኋቸው:: [5]ስለዚህ እረኛ የለምና ተበተኑ፤ በመበተናቸውም ለአራዊቱ ሁሉ መብል ሆኑ:: [6]በጎቼ በየተ ራራው ሁሉና በየኰረብታው ላይ ተንከራ ተቱ:: በምድር ሁሉ ተበተኑ፤ የፈለጋቸውም፣ የፈቀዳቸውም የለም::

[7]“ “ስለዚህ እናንት እረኞች፣ *የእግዚአ ብሔርን* ቃል ስሙ፤ [8]በሕያውነቴ እምላለሁ፣ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ እረኞቼ መንጋዬን ስላልፈለጉ ፣ ከመንጋዬም ይልቅ ራሳቸውን ስለተንከባከቡ፣ መንጋዬ እረኛ አጥቶ ለንጥ ቂያ ተዳርጎአል፤ ለአራዊትም ሁሉ መብል ሆኖአል:: [9]ስለዚህ እረኞች ሆይ፤ *የእግዚ አብሔርን* ቃል ስሙ፤ [10]ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ እኔ በእረኞች ላይ ተነሥቻለሁ፤

ነዋሪዎች ነው:: *አብርሃም አንድ ራሱን ብቻ ነበር ... እኛ ግን ብዙዎች ነን፤* ይህ አባባል፣ ንስሓ ያልገቡ ሰዎች የተናገሩት በትምክህት ነው፤ ይህም በ11+15 ላይ ከተገለጸው ጋር ተመሳሳይነት አለው (ከሉቃ3+8 ጋር ያነጻጽሩ)::

33+25 *ሥጋውን ከነደሙ ትበላላችሁ፤* በዘፍ 9+4፤ ዘሌ 7+26-27፤ 17+10፤ ዘዳ12+16:23 ላይ ግን የተከለከለ ነው:: *ዐይኖቻችሁንም ወደ ጣዖቶቻችሁ ታነሣላችሁ፤* የ18+6 ማብ ይመ::

33+27 *እኔ ሕያው እግዚአብሔርን፤ በራሴ እምላለሁ፤* የ18+3 ማብ ይመ:: *ለዱር አራዊት ... በቸነፈር፤* በ5+12፤ 7+15፤ 12+16፤ ላይ በሦስት ዐይነት መንገድ የተገለጠውን መቅ ሠፍትና በ14+12-21 በአራት ዐይነት የተገለጠውን መቅሠፍት ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ::

*33+30-33፤* ለሕዝቅኤል ብቻ የተነገረ ነው::

33+31 *ከፊትህ ይቀመጣሉ፤* ከዚህ በፊት ሽማግሌዎቹ እንዳደረጉት ማለት ነው (8+1፤ 14+1):: *ተገቢ ባልሆነ ጥቅም ላይ፤* ሕዝቡ ከሕዝቅኤል መስማት የሚፈልጉት በዚህ ሁኔታ ውስጥ ትርፍ የሚያገኙበትን መንገድ እንጂ፣ እግዚአብሔር ለእነርሱ ያለውን ትልቅ ዐላማ እንዲያሳውቃቸው አልነበረም (ከማቴ 20+20-28 ጋር ያነጻጽሩ)::

33+32 *ቃልህን ሰምተው ሥራ ላይ የማያውሉት፤* ኢሳ 29+13፤ ማቴ21+28-32 ይመ፤ ከያዕ1+22-25 ጋር ያነጻጽሩ:: *የሚዘፍን፤* ሕዝቅኤል ንግሩን በዜማ ማሰማቱን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (2ነገ3+15፤ ኢሳ5+1)፤ በይበልጥ ግን፣ ነቢዩ መል እክቱን ለማስተላለፍ በተለዋጭ ዘይቤ የተጠቀመ ይመስላል::

34+2 *በእስራኤል እረኞች፤* እነዚህ ሕዝቡን የመምራት ኀላፊነት የተሰጣቸው በተለይም ነገሥታትና ሹማምንቶቻቸው ናቸው (2ሳሙ7+7፤ ኤር25+18-19)፤ ይሁን እንጂ፣ ይህ ስም ነቢያትንና ካህናትንም ያካትታል (ኢሳ56+11፤ ኤር23+9-11 ይመ):: ቀደም ብሎ ሕዝቅኤል መሳፍንትን፣ ካህናትንና ነቢያትን በተናጠል ወቅሶአቸው ነበር (ም22):: ጥንት በመካከለኛው ምሥራቅ ንጉሥን፣ “እረኛ” ብሎ መጥራት የተለመደ ነበር:: ዳዊት ከበግ እረኝነት እንዴት የእግዚአብሔር ሕዝብ እረኛና ንጉሥ እንደሆነ መዝ78+70-71 ይመ፤ እረኞች ስለተገሠጹበት ጕዳይ ይህን ከኤር 23+1-4 ጋር ያነጻጽሩ::

34+3 *ትበላላችሁ ... ትለብሳላችሁ ... ዐረዳችሁ፤* መልበሳቸውም ሆነ ዐርደው መብላታቸው ለእረኞች የሚገባ ቢሆ ንም፣ ለመንጋው የሚያስፈልገውን እንክብካቤ አለማድረጋቸው ግን ወንጀለኛ አድርጎአቸዋል::

34+4 *የጠፉትንም አልፈለጋችሁም፤* ከኤር50+6፤ ማቴ 18+12-14፤ ሉቃ15+4፤ 19+10 ጋር ያነጻጽሩ::

34+5 *ተበተኑ፤* አብዛኛውን ጊዜ ሕዝቅኤል የእስራኤላ ውያንን መማረክና በየቦታው መበታተንን ለመግለጽ የሚጠቀ ምበት ቃል ነው (11+16-17፤ 12+15፤ 20+23:34:41፤ 22+15: 28+25):: *እረኛ የለምና፤* አብዛኛውን ጊዜ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሚገኝ ተለዋጭ ዘይቤ ነው (ለምሳሌ ማር6+34)::

34+8 *ለአራዊት፤* በእስራኤል ዙሪያ ያሉትን ጨካኝ ሕዝቦች ያመለክታል፤ በተጨማሪም በቍ28 ላይ ተነጻጽረው የተገለ

ስለ መንጋዬ እጠይቃቸዋለሁ፤ ከእንግዲህ እረኞች ራሳቸውን መመገብ እንዳይችሉ፣ መንጋዬን እንዳያስማሩ አደርጋለሁ። መንጋዬን ከአፋቸው አስጥላለሁ፤ ከእንግዲህም ምግብ አይሆናቸውም።

[11]" 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላልና፤ እኔ ራሴ በጎቼን እፈልጋቸዋለሁ፤ እጠብቃቸዋለሁም። [12]እረኛ ከመንጋው ጋር ሳለ፣ የተበተኑበትን በጎች እንደሚፈልግ ሁሉ፣ እኔም በጎቼን እፈልጋለሁ። በደመናና በጨለማ ቀን ከተበተኑበት ስፍራ ሁሉ አድናቸዋለሁ። [13]ከአሕዛብ መካከል አወጣቸዋለሁ፤ ከየአገሮቹ እሰበስባቸዋለሁ፤ ወደ ገዛ ምድራቸውም አመጣቸዋለሁ። በእስራኤል ተራሮች፣ በየወንዙ ዳርና፣ በምድሪቱ መኖሪያዎች ሁሉ እንዲሰማሩ አደርጋለሁ። [14]በመልካም ስፍራ አሰማራቸዋለሁ፤ የእስራኤል ተራሮች ከፍታም የግጦሽ መሬት ይሆናቸዋል። በመልካሙ ግጦሽ መሬት ላይ ይተኛሉ፤ እዚያም በእስራኤል ተራሮች ለምለም መስክ ላይ ይመገባሉ። [15]እኔ ራሴ በጎቼን አሰማራለሁ፤ አስመስጋቸዋለሁም። ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*። [16]የጠፉትን እፈልጋለሁ፤ የባዘኑትንም እመልሳለሁ። የተጐዱትን እጠግናለሁ፤ የደከሙትንም አበረታለሁ፤ የወፈረውንና የበረታውን ግን አጠፋለሁ። መንጋውን በፍትሕ እጠብቃለሁ።

[17]" '*መንጋዬ* ስለ ሆናችሁት ስለ እናንተ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በበግና በበግ መካከል፣ በአውራ በግና በአውራ ፍየል መካከል እፈርዳለሁ። [18]በለምለሙ መስክ ላይ መመገቡ አይበቃችሁምን? የተረፈውን መሰማሪያችሁን ደግሞ በእግራችሁ መረጋገጥ ይገባችኋልን? ንጹሕ ውሃ መጠጣቱ አይበቃችሁምን? የተረፈውንስ በእግራችሁ ማደፍረስ ይገባችኋልን? [19]*መንጋዬ* የረጋገጣችሁትን መመገብና በእግራችሁ ያደፈረሳችሁትን መጠጣት ይገባዋልን?

[20]" 'ስለዚህ ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላቸዋል፤ "እነሆ እኔ ራሴ በሰባው በግና በከሳው በግ መካከል እፈርዳለሁ። [21]ደካሞቹን በጎች በጐናችሁና በትከሻችሁ ስለምትገፈትሩ፣ እስኪባረሩም ድረስ በቀንዳችሁ ስለምትወጓቸው፣ [22]እኔ *መንጋዬን* አድናለሁ፤ ከእንግዲህ ለንጥቂያ አይዳረጉም፤ በአንዱ በግና በሌላውም በግ መካከል እፈርዳለሁ። [23]በእነርሱ ላይ አንድ እረኛ፣ ባሪያዬን ዳዊትን አቆማለሁ፤ እርሱም ያሰማራቸዋል፤ እረኛቸውም ይሆናል። [24]እኔ *እግዚአብሔር* አምላካቸው እሆናለሁ፤ ባሪያዬ ዳዊትም በመካከላቸው ገዥ ይሆናል፤ እኔ *እግዚአብሔር* ተናግሬአለሁ።"

[25]" 'ከእነርሱ ጋር የሰላም ቃል ኪዳን እገባለሁ፤ ከዚያም ምድሪቱን ከዱር አራዊት ነጻ አደርጋለሁ፤ እነርሱም በምድረ በዳ ይኖራሉ፤ በደንም ውስጥ በሰላም ይተኛሉ። [26]እነርሱንና በኰረብታዬ ዙሪያ ያሉትን ስፍራዎች እባርካለሁ።[a] በወቅቱም ዝናብ አወርድላቸዋለሁ፤ ዝናቡም የበረከት ዝናብ ይሆናል። [27]የየሜዳው ዛፍ ፍሬ ይሰጣል፤ መሬቱም እህል ያበቅላል። ሕዝቡም በምድሪቱ ላይ በሰላም ይኖራሉ። የቀንበሮቻቸውን ማነቆ ሰብሬ በባርነት ከገዟቸው እጅ ሳድናቸው፣ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ

34፥10 1ሳሙ2፥29-30፤መዝ72፥14፤ ኤር21፥13፤23፥2፤ ዘካ10፥3
34፥11 መዝ119፥176
34፥12 ኢሳ40፥11፤ ኤር31፥10፤ሕዝ32፥7፤ዘካ10፥3፤ሉቃ19፥10
34፥13 ዘፍ48፥21፤ ዘዳ30፥4፤ኢሳ66፥20፤ ኤር23፥3፡8፤50፥19፤ ሕዝ11፥17፤28፥25፤ 36፥24፤ሚክ4፥6
34፥14 መዝ23፥2፤ 37፥3፤ኢሳ65፥10፤ ሕዝ20፥40፤36፥29-30፤37፥22፤አሞ9፥14፤ሚክ7፥14
34፥15 መዝ23፥1-2፤ኤር33፥12፤ሚክ5፥4፤ሶፎ3፥13
34፥16 መዝ147፥3፤ ኢሳ10፥16፤ኤር31፥8፤ሚክ4፥6፤ሶፎ3፥19፤ ሉቃ5፥32፤19፥10
34፥17 ማቴ25፥32-33
34፥18 ዘፍ30፥15፤ ሕዝ32፥2
34፥20 ማቴ25፥32
34፥21 ዘዳ33፥17
34፥22 መዝ72፥12-14፤ ኤር23፥2-3፤ሕዝ20፥37-38
34፥23 ኢሳ31፥4፤ 40፥11፤ሚክ5፥4
34፥24 መዝ89፥49፤ ኢሳ53፥4፤ኤር23፥4-5፤30፥9፤33፥14፤ ሕዝ36፥28፤ዘካ13፥7፤ ዮሐ10፥16፤ራእ7፥17
34፥25 ዘሌ25፥18፤ 26፥6፤ዘኍ25፥12፤ ኢሳ11፥6-9፤ሕዝ16፥62፤ሆሴ2፥18
34፥26 ዘፍ12፥2፤ ዘዳ11፥13-15፤28፥12፤መዝ68፥9፤ኢሳ44፥3፤ ኢዩ2፥23
34፥27 ዘሌ26፥13፤ ዘኍ24፥21፤ኢዮ14፥9፤ መዝ67፥6፤ 72፥16፤ ኤር30፥8፤ሕዝ20፥42፤28፥25

[a]26 *ወይም እነርሱንና በኰረብታዬ ዙሪያ ያሉትን ስፍራዎች በረከት አደርጋቸዋለሁ*

ጹበትን ይመ።

34፥10 *እኔ በእረኞች ላይ ተነሥቻለሁ፤* የ5፥8 ማብ ይመ።

34፥11 *እኔ ራሴ በጎቼን እፈልጋቸዋለሁ፤* ታማኞች ያልሆኑትን እረኞች ከወቀሰ በኋላ (ቍ 1-10)፣ ከእንግዲህ ወዲህ ግን የበጎቹ ጠባቂ ራሱ እግዚአብሔር መሆኑን ይገልጻል። (ኤር 23፥3-4 ይመ)።

34፥12 *ከተበተኑበት ስፍራ ሁሉ፤* እስራኤላውያን በምርኮ የሄዱት ወደ ባቢሎን ብቻ አልነበረም (ኤር43፥1-7 ይመ)። *በደመናና በጨለማ ቀን፤* ነሐሴ 586 ዓ.ቅ.ክ. ኢየሩሳሌም በወደቀች ጊዜ፣ የእግዚአብሔር ቀን በእስራኤል ላይ መምጣቱን ያመለከተ ነበር (7፥7 እና ማብ ይመ)።

34፥13 *አወጣቸዋለሁ፤* እንደ ገና የመመለሳቸው ተስፋ በ11፥17 ላይ መሳት ተጀመረ፤ በ20፥34፡41-42፤ 28፥25 ላይ ተስፋው ተደገመ፤ በዚህኛው የሕዝቅኤል መጽሐፍ ክፍልም ልዩ ትኵረት ተሰጠው (ም33-39)፤ 36፥24፤ 37፥21፤ 38፥8፤ 39፥27 ይመ። *በእስራኤል ተራሮች፤* በቍ 12 የተገለጸውን ፍርድ፣ በ6፥3-7 ከተገለጸው ጋር ያነጻጽሩ። ምናልባት ተራሮቹ የሚያመለክቱት የድነትን ሁኔታ ሊሆን ይችላል።

34፥14 *አሰማራቸዋለሁ፤* ኢሳ40፥11፤ ዮሐ10፥11 ይመ።

34፥16 *የወፈረውንና የበረታውን፤* ሌሎች በጎችን ጨቍነው፣ ራሳቸውን ያወፈሩ ባለሥልጣናትን ነው (ቍ 17-22 ይመ)።

34፥17 *በአውራ በግና በአውራ ፍየል፤* ድኾች እስራኤላውያንን የሚጨቁኑ፣ ኀይልና ሥልጣን ያላቸውን ሰዎች የሚያመለክት ነው። በነቢያት መጽሐፍት ይህ የትንቢት ቃል፣ ማኅበራዊ ፍትሕን በተመለከተ ተጠቅሶ ይገኛል (ኢሳ3፥13-15፤ 5፥8፤ አሞ5፥12፤ 6፥1-7፤ ሚክ2፥1-5 ይመ)፤ ይህን ኤርምያስ በአንክሮ ከተመለከተው፣ ከባሪያዎች ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ (ኤር 34፥8-11)።

34፥23 *ባሪያዬን ዳዊትን፤* እንደ ዳዊት ያለ ከእርሱ ዘር የሆነ ገዥ ማለት ነው (መዝ89፥4፡20፡29፤ ኤር23፥5-6 ይመ)።

34፥24 *ገዥ፤* የእግዚአብሔር መንግሥት በምድር ላይ የምትመሠረትበትና ንጉሡም እርሱ ራሱ እንደሚሆን ያመለክታል፤ በዚህ ጊዜም ምድራውያን ነገሥታት ገዥ ይሆናሉ (ከ37፥25፤ 44፥3፤ 45፥7፡16-17፡22፤ 46፥2-18፤ 48፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ።

34፥25 *የሰላም ቃል ኪዳን፤* ከ37፥26 ጋር ያነጻጽሩ። የእግዚአብሔር ቃል ኪዳን ሁሉ ዐላማ የሚያደርገው ሰላምን ነው (ዘፍ26፥28-31፤ ዘኍ25፥12፤ ኢሳ54፥10፤ ሚል2፥5 ይመ)። ይህ ቃል ኪዳን በኤር31፥31-34 ላይ፣ "አዲስ ኪዳን" ተብሎ የቀረበ ሲሆን፣ ይህም በክርስቶስ የተጀመረና (ፊል4፥7)፣ሙሉ በሙሉም እንደሚፈጸም የሚጠበቅ ነው። ይህ በዕብራይስጥ፣ "ሻሎም" ተብሎ የሚተረጐመው ሰላም፣ ጠላትነት እንዳልነበር ከሚሆንበት በላይ፣ የሕይወትን ሙላት፣ ሥጋት በሌለበት ሁኔታ በደስታ መኖርን ያመለክታል። *በደንም ውስጥ ... ይተኛሉ፤* አብዛኛውን ጊዜ አደገኛ በሆነ ደን ውስጥ እንኳ፣ ሰላም ይኖራል ማለት ነው (መዝ104፥20-21፤ ኤር5፥6 ይመ)።

34፥26 *በወቅቱም ዝናብ አወርድላችኋለሁ፤* ይህም የክረምቱን መግባት የሚያበስር የበልግ ዝናብና ክረምቱ ከወጣ በኋላም የሚተካውን የጸደይን ዝናብ ነው (ከኤር5፥24 ጋር ያነጻጽሩ)። *የበረከት ዝናብ፤* ይህ በረከት በአብርሃም አማካይነት ለእግዚአብሔር ሕዝብ የተሰጠ የሕይወት ኀይል ተስፋ ሲሆን (ዘፍ12፥1-3)፣ ሕይወት በሚሰጥ ዝናብ ተመስሎ በሚገባ ቀርቦአል።

34፥27 *የቀንበሮቻቸውን ማነቆ፤* ቀንበር ከዕንጨት የሚሠራ ሲሆን፣ በከብት ዐንገት ላይ በሚያርፈው ቀንበር ቀዳዳዎች

ያውቃሉ:: [28]ከእንግዲህ ለሌሎች ሕዝቦች ንጥቂያ አይዳረጉም፤ የዱር አራዊት አይበ ጫጭቋቸውም፤ በሰላም ይኖራሉ፤ የሚያስ ፈራቸውም አይኖርም:: [29]ከእንግዲህ በምድሪቱ ላይ የራብ ተጠቂ እንዳይሆኑ፣ የአሕዛብንም ስድብ እንዳይሸከሙ ፍሬ በመስጠት የታወ ቀውን መሬት እሰጣቸዋለሁ:: [30]ከዚያም እኔ እግዚአብሔር አምላካቸው ከእነርሱ ጋር እንደ ሆንሁ፤ የእስራኤል ቤት የሆኑት እነርሱም ሕዝቤ እንደ ሆኑ ያውቃሉ፣ ይላል ጌታ እግዚአብሔር:: [31]እናንተ በጎቼ የማሰማሪያዬ በጎች ያልኋችሁ፣ ሕዝብ ናችሁ፤ እኔም አምላካችሁ ነኝ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር::

## በኤዶም ላይ የተነገረ ትንቢት

**35** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [2]"የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን ወደ ሴይር ተራራ አዙር፤ ትንቢትም ተናገርበት፤ [3]እንዲህም በል፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ የሴይር ተራራ ሆይ፤ በአንተ ላይ ተነሥቻለሁ፤ እጄን በአንተ ላይ እዘረጋለሁ፤ ባድማና ጠፍ አደርግሃለሁ:: [4]ከተሞችህን ፍርስራሽ አደርጋቸዋለሁ፤ ባድማ ትሆናለህ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቃለህ::

[5]" 'እስራኤላውያን ቅጣታቸው እጅግ መራራ ከሆነ ደረጃ ላይ ደርሶ ፍዳቸውን በሚቀበሉበት ጊዜ፣ የጥንቱን ቂም ቋጥረህ ለሰይፍ ስለ ዳረግሃቸው፤ [6]በሕያውነቴ እምላለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ ለደም ማፍሰስ አሳልፌ እሰጥሃለሁ፤ እርሱም ያሳድድሃል:: ደም ማፍሰስን ስላልጠላህ፣ ደም ማፍሰስ ያሳድድሃል:: [7]የሴይርን ተራራ ባድማና ጠፍ አደርጋለሁ፤ በእርሱም ላይ የሚወጡትንና የሚወርዱትን አስቀራለሁ:: [8]ተራሮችህን በሬሳ እሞላለሁ፤ በሰይፍ የተገደሉት ሁሉ በተራሮችህ፣ በሸለቆዎችህና በውሃ መውረጃዎችህ ሁሉ ላይ ይወድቃሉ:: [9]ለዘላለም ባድማ አደርግሃለሁ፤ ከተሞችህ መኖሪያ አይሆኑም:: ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ::

[10]" 'እኔ እግዚአብሔር በዚያ እያለሁ፣ "እነዚህ ሁለት ሕዝቦችና ሁለት አገሮች የእኛ ይሆናሉ፤ እኛም እንወርሳቸዋለን::" ብለሃልና፤ [11]ስለዚህ በሕያውነቴ እምላለሁ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ ከጥላቻችሁ የተነሣ በእነርሱ ላይ በገለጣችሁት ቍጣና ቅናት ልክ እፈርድባችኋለሁ፤ በእናንተም ላይ በምፈርድበት ጊዜ፣ ማንነቴ በእነርሱ መካከል እንዲታወቅ አደርጋለሁ:: [12]ከዚያም ስለ እስራኤል ተራሮች፣ "ጠፍ ሆነዋል፤ ቦጫጭቀን እንድንበላቸው ለእኛ ተሰጥተዋል" ብለህ በንቀት የተናገርኸውን እኔ እግዚአብሔር እንደ ሰማሁ በዚያን ጊዜ ታውቃለህ:: [13]በእኔ ላይ ታብየሃል፤ በድፍረትም በእኔ ላይ ተናግረሃል፤ እኔም ሰምቼዋለሁ:: [14]ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ መላዪቱ ምድር በምትደሰትበት ጊዜ አንተን ባድማ አደርግሃለሁ:: [15]የእስራኤል ቤት ርስት ባድማ በሆነች ጊዜ ስለ ተደሰትህ፣ እኔም እንዲሁ አደርግብሃለሁ:: የሴይር ተራራ ሆይ፤ አንተና መላዋ ኤዶም ባድማ ትሆናላችሁ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::

## ለእስራኤል ተራሮች የተነገረ ትንቢት

**36** "የሰው ልጅ ሆይ፤ ለእስራኤል ተራሮች ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በል፤ 'የእስራኤል ተራሮች ሆይ፤ የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ:: [2]ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ጠላት ስለ አንቺ፣ 'እሰይ! እነዚያ የጥንት ተራሮች የእኛ ርስት ሆነዋል' ብሎአል::"' [3]ስለዚህ ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በል፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ከየአቅጣጫው ከበው በመውጋት ስላጠቋችሁ፣ ለቀሩት ሕዝቦች ሁሉ ርስት ሆናችሁ፤

34+28 ኤር30+10፤ 32+37፤ሕዝ28+26፤ 39+26፤ሆሴ11+11፤ አሞ9+15፤ሶፎ3+13፤ ዘካ14+11
34+29 መዝ137+3፤ ኢሳ4+2፤ሕዝ36+6: 15:29፤ኢዩ2+19
34+30 ሕዝ14+11፤ 37+27
34+31 መዝ28+9፤ ኤር23+1
35+2 ዘፍ14+6
35+3 ኢሳ34+10፤ ኤር6+12፤ሕዝ 25+12-14
35+4 ቍ9፤ኤር 44+2፤49+10
35+5 መዝ63+10፤ 137+7፤ሕዝ21+29፤ አብ1+13
35+6 ኢሳ34+3፤ 63+2-6
35+7 ኤር46+19፤ 49+17
35+8 ሕዝ31+12
35+9 ኢሳ34+5-6፤ ኤር49+13፤ አብ1+10
35+10 መዝ83+12፤ ሕዝ36+2:5
35+11 መዝ9+16፤ ሕዝ25+14፤አብ1+15፤ ማቴ7+2
35+12 ኤር50+7
35+13 ኤር49+16፤ ዳን11+36
35+14 ኤር51+48
35+15 ቍ3፤ ኢሳ 34+5-6:11፤ ኤር50+11-13፤ ሰቆ4+21፤ሕዝ32+29፤ 36+5፤አብ 1+12
36+1 ሕዝ17+22
36+2 ዘዳ32+13፤ ሕዝ6+2-3፤25+3፤ 35+10
36+3 መዝ44+13 -14፤ሰቆ2+16፤3+62፤ አብ1+13

ውስጥ ቍልቍል ወርደው ጫፍና ጫፋቸው በገመድ ይታሰራል (ኢሳ 58+6 ይመ፤ ከ30+18፤ ዘሌ26+13፤ ኤር27+2፤ 28+10-13 ጋር ያነጻጽሩ):: ሥዕላዊ አገላለጹ በአጠቃላይ የሚያሳየው፣ በወራሪ ኀይል ሥር መሆንን ነው::

34+29 *የአሕዛብንም ስድብ፤* 22+4 ይመ::

34+30 *እኔ እግዚአብሔር አምላካቸው ከእነርሱ ጋር እንደ ሆንሁ፣ ... እነርሱም ሕዝቤ እንደ ሆኑ፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የነዚህ ዐይነት ተጓዳኝ ሐረጐች ባይኖሩም፣ ነገሩ የቃል ኪዳን አባባል ነው (ከ11+20፤ ዘፀ6+7፤ ሆሴ1+9 ጋር ያነጻጽሩ)::

35+2 *ፊትህን ... አዙር፤* የ20+46 ማብ ይመ:: *በሴይር ተራራ፤* ኤዶም ማለት ነው፤ ይህም ከእስራኤል ሕዝብ ጋር የሥጋ ዝምድና የዐጥንት ፍላጭ ነው (ቍ15፤ ዘፍ25+21-30 ይመ):: ኤዶም ወገናቸው ስለ ነበር፣ እስራኤላውያን ወንድምነቱን ፈለጉ፤ ነገር ግን አልተሳካላቸውም (ከአሞ1+11 ጋር ያነጻጽሩ):: እስራኤል ሰላም ከማግኘቷ በፊት፣ ኤዶም መቀጣት ነበረባት (ከዘፍ32-33 ጋር ያነጻጽሩ)፤ 25+12 እና ማብ ይመ፤ ኢሳ63+1-6 ይመ::

35+3 *በአንተ ላይ ተነሥቻለሁ፤* የ5+8 ማብ ይመ::

35+5 *የጥንቱን ቂም፤* ዔሳው መቀበል የነበረበትን በረከት ያዕቆብ ለማግኘት ሲል አባቱን ይስሐቅን ካታለለበት ጊዜ ጀምሮ፣ (ዘፍ27)፤ ይህ ጥላቻ እስከዚህ ጊዜ ድረስ ነበር (ዘኍ 20+14-21 2ሳሙ8+13-14፤ 1ነገ9+26-28):: *ፍዳቸውን በሚቀበሉበት ጊዜ፤* በ586 ዓ.ቅ.ክ. ኤዶም ኢየሩሳሌምን ዘረፈች፤ በዚሁ ጊዜም ከባቢሎናውያን ጋር በመተባበር እስራኤላውያን ምርኮኞችን ገደለች፤ ከመሬታቸውም ጥቂቱን ወረሰች (ቍ10)፤ አብ11-14 ይመ::

35+6 *እኔ ሕያው እግዚአብሔርን! በራሴ እምላለሁ፤* የ18+3 ማብ ይመ:: *ደም ማፍሰስ ያሳድድሃል፤* በዘፍ9+6 መሠረት የተላለፈ ፍርድ ነው::

35+9 *ለዘላለም ባድማ፤* እንደ ግብፅ ሁሉ ኤዶምም ተመልሳ አትሠራም (29+13-16 ይመ)::

35+10 *እነዚህ ሁለት ሕዝቦች፤* እስራኤልንና ይሁዳን ማለት ነው::

35+11 *እኔ ሕያው እግዚአብሔርን! በራሴ እምላለሁ፤* የ18+3 ማብ ይመ::

35+13 *በእኔ ላይ ታብየሃል፤* ከአብ12፤ ሶፎ2+8:10 ያነጻጽሩ:: እንዲሁም ከመዝ35+26፤ ኤር48+26:42 ጋር ያነጻጽሩ::

*36+1-15፤* በም6 ከተገለጸው ይልቅ፣ ይኸኛው በተቃራኒ የቀረበ ነው፤ ከቍ1-7 ያለው በአሕዛብ ላይ ስለሚመጣው ፍርድ ሲሆን፣ ከቍ8-15 ያለው ደግሞ የእስራኤልን ከምርኮ መመለስ ያመለክታል::

36+2 *ጠላት ... ብሎአል፤* 25+3፤ 26+2 ይመ:: *እሰይ፤* የ25+3 ማብ ይመ:: *የጥንት ተራሮች፤* እነዚህ በዮርዳኖስ ሸለቆና በሜድትራኒያን ጠረፍ መካከል ያሉ፣ ከፍተኛ ቦታዎች ናቸው፤ ይህችም የተስፋዪቱ ናት::

36+3 *ለቀሩት ሕዝቦች፤* በመጨረሻም ድል አድርገው

ለሕዝብም መሣቂያና መሣለቂያ ሆናችሁ::" [4]ስለዚህ የእስራኤል ተራሮች ሆይ፤ የጌታ እግዚአብሔርን ቃል ስሙ፤ ጌታ እግዚአብሔር ለተራሮችና ለኰረብቶች፣ ለሸለቆዎችና ለውሃ መውረጃዎች፣ ለፈራረሱ ባድማዎችና፣ በሌሎቹ በዙሪያችሁ ባሉት ሕዝቦች ተዘርፈውና መዘባበቻ ሆነው መና ለቀሩት ከተሞች እንዲህ ይላል፤ [5]ልዑል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "በሚቃጠል ቅናቴ በቀሩት ሕዝቦች ሁሉና በኤዶም ሁሉ ላይ ተናግሬአለሁ፤ ከልብ በመነጨ ደስታና በንቀት ተሞልተው የግጦሽ መሬቴን ይዘው ይበዘብዙት ዘንድ የራሳቸው ርስት አድርገውታልና::" [6]ስለዚህ የእስራኤልን ምድር የሚመለከት ትንቢት ተናገር፤ ለተራሮች፣ ለኰረብቶች፣ ለሸለቆዎችና ለውሃ መውረጃዎች እንዲህ በል፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "በሕዝቦች ዘለፋ ስለ ተሠቃያችሁ ቍጣ በተሞላ ቅናቴ እናገራለሁ::" [7]ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "እጄን አንሥቼ እምላለሁ፤ በዙሪያችሁ ያሉ ሕዝቦች ዘለፋ ይወርድባቸዋል::"

[8]" 'የእስራኤል ተራሮች ሆይ፣ እናንተ ግን፤ ለሕዝቤ ለእስራኤል ቅርንጫፍ ታወጣላችሁ፤ ፍሬም ታፈራላችሁ፤ በቅርቡ ወደ አገራቸው ይመለሳሉና:: [9]ስለ እናንተ ይገደኛል፤ በበጎነትም እመለከታችኋለሁ፤ ትታረሳላችሁ፤ ዘርም ይዘራባችኋል:: [10]መላው የእስራኤል ቤት እንኳ ሳትቀሩ፣ የሰዎችን ቍጥር በእናንተ ላይ አበዛለሁ:: ከተሞች የሰው መኖሪያ ይሆናሉ፤ የፈረሱት እንደ ገና ይሠራሉ:: [11]በእናንተ ላይ የሰዎችንና የእንስሳትን ቍጥር እጨምራለሁ፤ ፍሬያማ ይሆናሉ፤ ቍጥራቸውም ይበዛል:: እንዳለፈው ጊዜ ሁሉ ሰዎች በውስጣችሁ እንዲኖሩ አደርጋለሁ፤ ካለፈው የበለጠ አበለጽጋችኋለሁ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ:: [12]ሰዎችን፣ ሕዝቤን እስራኤልን በእናንተ ላይ እንዲመላለሱ አደርጋለሁ፤ ይወርሷችኋል፤ እናንተም ርስታቸው ትሆናላችሁ፤ ከእንግዲህ ወዲህ ልጅ አልባ አታደርጓቸውም::

[13]" 'ልዑል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ሕዝቡ እናንተን፣ 'ሰዎችን ቦጫጭቀው ይበላሉ፤ ሕዝብንም ልጅ አልባ ያደርጋሉ' ስላሏችሁ፣ [14]ከእንግዲህ ሰው አትበሉም፤ ሕዝቡንም ልጅ አልባ አታደርጉትም፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር:: [15]ከእንግዲህ የሕዝቦችን ዘለፋ እንድትሰሙ አላደርግም፤ በሰዎችም ስድብ አትሠቃዩም፤ ከእንግዲህ ለሕዝባችሁ መሰናከል አትሆኑም፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር::"

[16]እንደ ገና የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [17]የሰው ልጅ ሆይ፤ የእስራኤል ሕዝብ በገዛ ምድራቸው ይኖሩ በነበረበት ጊዜ በሥራቸውና በአኗኗራቸው አረከሷት፤ ጠባያቸውም በፊቴ፣ ሴት በወር አበባዋ ወቅት እንደምትረክሰው ዐይነት ነበር:: [18]ስለዚህ በምድሪቱ ላይ ደም ስላፈሰሱና በጣዖታቶቻቸው ስላረከሷት፣ መዓቴን አፈሰስሁባቸው:: [19]በአሕዛብ መካከል በተንኋቸው፤ እነርሱም በየአገሩ ተበታተኑ፤ እንደ ጠባያቸውና እንደ ሥራቸው መጠን ፈረድሁባቸው:: [20]በአሕዛብ መካከል በሄዱበት ሁሉ ቅዱስ ስሜን አረከሱ፤ ስለ እነርሱ፣ 'እነዚህ የእግዚአብሔር ሕዝብ ናቸው፤ ዳሩ ግን የእርሱን ምድር ትተው እንዲሄዱ ተገደዱ' ተብሎአልና:: [21]የእስራኤል ቤት በሄዱበት በአሕዛብ መካከል ሁሉ፣ ስላረከሱት ቅዱስ ስሜ ገዶኛል::

[22]"ስለዚህ ለእስራኤል ቤት እንዲህ በል፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "የእስራኤል ቤት ሆይ፤ ይህን ሁሉ የማደርገው ስለ እናንተ ብዬ ሳይሆን፣ በየሄዳችሁባቸው

36፥4 ዘሌ26፥43፤ ዘዳ11፥11፤መዝ79፥4፤ ኤር2፥26፤ሕዝ6፥3፤ 33፥24፡28-29
36፥5 ዘዳ29፥20፤ ኢሳ66፥16፤ኤር25፥31፤50፥11፤ሕዝ25፥12-14፤35፥10፡15፤ 38፥22፤ኢል3፥2፡14
36፥6 መዝ123፥3-4፤ሕዝ34፥29
36፥7 ዘኍ14፥30፤ ኤር25፥9
36፥8 ኢሳ4፥2፤ 27፥6፤ሕዝ47፥12
36፥9 ቍ34-36፤ ኤር31፥27
36፥10 ኢሳ49፥8፡ 17-23፤ኤር30፥18
36፥11 ዘፍ1፥22፤ ዘሌ26፥9፤ኢዮ42፥13፤ ኢሳ49፥19፤ ኤር31፥28፤ ሕዝ16፥55፤ ሚክ7፥14፤ዘካ10፥8
36፥12 ሕዝ47፥14፡ 22
36፥13 ዘኍ13፥32
36፥15 መዝ89፥50-51፤ኢሳ54፥4፤ ሕዝ34፥29
36፥17 ዘሌ5፥2፤ 12፥2፤መዝ106፥37-38፤ኤር2፥7
36፥18 2ዜና34፥21
36፥19 ዘሌ18፥24-28፤ዘዳ28፥64፤ሕዝ 7፥8፤24፥14፤39፥24
36፥20 ዘሌ18፥21፤ ኢሳ52፥5፤ኤር33፥24፤ሕዝ12፥16፤13፥19፤ ሮሜ2፥24
36፥21 መዝ74፥18፤ ኢሳ48፥9
36፥22 ዘዳ9፥5-6፤ መዝ106፥8፤ኢሳ37፥35፤ሕዝ20፥9፡44፤ ሮሜ2፥24

ሙሉ በሙሉ ከመያዛቸው በፊት፣ እስራኤልን በመውረር በከፊል የያዟትን ማለት ነው::

36፥4 *ለተራሮችና ለኰረብቶች፣ ለሸለቆዎችና ለውሃ መውረጃዎች፤* የ1፥5 ማብ እና 6፥3 ይመ::

36፥5 *በሚቃጠል ቅናቴ፤* ለእርሱ ለራሱ የሆነችውን ምድር ፣ አሕዛብ ስለሰደቧት እግዚአብሔር ክፉኛ ተቈጥቶአል:: *ኤዶም፤* ለአያሌ ዘመናት የእስራኤል ጠላት ስለ ነበሩ፣ ከሌሎቹ ይልቅ ስማቸው ተለይቶ ተጠቅሶአል (35፥2፡5 ማብ ይመ)::

36፥7 *እጄን አንሥቼ፤* 20፥5 እና ማብ ይመ::

36፥8 *ቅርንጫፍ ... ፍሬም፤* እነዚህ የምርታማነትና የእግዚአብሔር ምሕረት ምልክቶች ናቸው (17፥8፡23)፣ ዘሌ26፥3-5 ይመ፤ በ35፥3፡7፡15 ላይ ስለ ኤዶም መፈራረስ ከተገለጸው ጋር የሚነጻጸር ነው:: *በቅርቡ፤* ፍርዱ ሳይዘገይ እንደሚፈጸምና ምርኮኞችም እንዲሁ (7፥7፤ 12፥23) የተሰደዱት ፈጥነው ወደ አገራቸው እንደሚመለሱ የተነገረ ነው::

36፥9 *በበጎነትም እመለከታችኋለሁ፤* በዘሌ26፥9 ላይ ከተገለጸው ተመሳሳይ ዐውድና ሐረግ ጋር ያነጻጽሩ::

36፥10 *መላው የእስራኤል ቤት እንኳ፤* ሕዝቅኤል በዚህ ምዕራፍ ላይ የእስራኤልን ከምርኮ መመለስ እንደተናገሩ ሁሉ፣ በ37፥15-23 ላይም ይህንኑ ሐሳብ ይገልጻል::

36፥11 *ፍሬያማ ይሆናሉ፤ ቍጥራቸውም ይበዛል፤* ይህ ሐረግ የያዘው ፍሬ ሐሳብ፣ በሥነ ፍጥረት ጊዜ የተሰጠውን መለኰታዊ ባርኮትና (ዘፍ1፥22፡28፤ 8፥17፤ 9፥1፡7ይመ):: እንዲሁም ከዚያ በኋላ በተከታታይ ከተሰጠው የኪዳን ባርኮት ጋር (ዘፍ17፥6፤ 35፥11፤ 48፥3-4፤ ዘፀ1፥7 ይመ):: *እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ፤* እነዚህ ቃላት የእግዚአብሔር ማንነቱ የሚታወቅባቸው ሲሆኑ፣ በዚህ መጽሐፍ ውስጥም የሚገኙና፣ የእግዚአብሔርን በፍርድ መገለጥ ቢያሳዩም፣ እዚህ ቍጥር ላይ ግን እግዚአብሔር በማዳን ሥራው ራሱን የገለጠበትን ሁኔታ የሚያመለክቱ ናቸው (የ5፥13 ማብ ይመ፤ ከ34፥30 ጋር ያነጻጽሩ)::

36፥12 በእናንተ ላይ እንዲመላለሱ፤ እዚህ ላይም ለእስራኤል ተራሮች ነው:: *ልጅ አልባ አታደርጓቸውም፤* እስራኤላውያን ምርኮኛ በመሆን የገዛ ራሳቸውን ሕልውና እንዲያጡ አስተዋጽዖ ያደረጉት፣ በዘይቤያዊ አገላለጽ፣ "ተራሮች" ተብለው የተጠሩት ናቸው፤ እነዚህ ተራሮች በፖለስቲና የነበሩትን ከነዓናውያንና የአምልኮ ማዕከሎቻቸውን ("የማምለኪያ ኰረብታዎች") ያመለክታሉ፤ እነዚህም እስራኤልን ያሳቱና የእግዚአብሔር ቍጣ በሕዝቡ ላይ እንዲወርድ ምክንያት የሆኑ ናቸው (6፥3 እና ማብ ይመ)::

*36፥16-38፤* እስራኤልን በተመለከተ፣ ሕዝቅኤል የተነበየውን ሁሉ ያጠቃልላል::

36፥18 *ደም ስላፈሰሱና በጣዖታቶቻቸው ስላረከሷት፤* በእስራኤል ስለ ነበረው ማኅበራዊ ኢፍትሐዊነትና ጣዖት የማምለክ ልምምዶችን የሚያመለክት ነው (22፥3 እና ማብ ይመ):: *በጣዖታቶቻቸው፤* የ6፥4 ማብ ይመ::

36፥20 *ቅዱስ ስሜን አረከሱ፤* እስራኤላውያን ከምድራቸው የተፈናቀሉት፣ አምላካቸው ሕዝቡን መጠበቅና መንከባከብ ካለመቻሉ የተነሣ ነው ብለው አስበው ነበር (ከዘኍ14፥15-16፤ 2ነገ18፥32-35፤ 19፥10-12 ጋር ያነጻጽሩ)::

አሕዛብ መካከል ስላረከሳችሁት ስለ ቅዱስ ስሜ ስል ነው:: [23]በአሕዛብ መካከል የረከሰ ውን፣ እናንተ በእነርሱ ዘንድ ያረከሳችሁ ትን ፣ የታላቁን ስሜን ቅድስና አሳያለሁ፤ ከዚያም ዐይኖቻቸው እያዩ፣ በእናንተ አማ ካይነት ራሴን ቅዱስ አድርጌ ስገልጥ፣ አሕ ዛብ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያው ቃሉ፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር::"

[24]" 'ከአሕዛብ መካከል አስወጣችኋለሁ፤ ከየአገሩ ሁሉ እሰበስባችኋለሁ፤ ወደ ገዛ ምድ ራችሁም መልሼ አመጣችኋለሁ:: [25]ንጹሕ ውሃ እረጫችኋለሁ፤ እናንተም ንጹሕ ትሆ ናላችሁ፤ ከርኵሰታችሁ ሁሉና ከጣዖታቶቻ ችሁ ሁሉ አነጻችኋለሁ:: [26]አዲስ ልብ እሰ ጣችኋለሁ፤ አዲስ መንፈስም በውስጣችሁ አሳድራለሁ፤ የድንጋይ ልባችሁን ከእናንተ አስወግዳለሁ፤ የሥጋንም ልብ እሰጣችኋለሁ:: [27]መንፈሴን በውስጣችሁ አሳድራለሁ፤ ሥርዐ ቴን እንድትከተሉና ሕጌን በጥንቃቄ እንድ ትጠብቁ አደርጋለሁ:: [28]ለቀድሞ አባቶቻችሁ በሰጠኋቸው ምድር ትኖራላችሁ፤ ሕዝቤም ትሆናላችሁ፤ እኔም አምላክ እሆናችኋለሁ:: [29]ከርኵሰታችሁ ሁሉ አነጻችኋለሁ፤ እህሉን አጠራለሁ፤ አበዛዋለሁም፤ ራብንም አላመ ጣባችሁም:: [30]ከራብ የተነሣ በአሕዛብ መካ ከል በውርደት እንዳትሳቀቁ፣ የዛፉን ፍሬና የዕርሻውን ሰብል አበዛለሁ:: [31]ከዚያም ክፉ መንገዳችሁንና የረከሰ ሥራችሁን ታስታው ሳላችሁ፤ ስለ ኀጢአታችሁና ስለ አስጸያፊ ድርጊታችሁ ራሳችሁን ትጠላላችሁ:: [32]ለእናንተ ስል ይህን እንደማላደርግ እንድ ይላል ጌታ እግዚአብሔር:: የእስ ቤት ሆይ፤ በአድራጎታችሁ ዕፈሩ፤ ተሸ ቀቁም!

[33]" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ከኀጢአታችሁ ሁሉ በማነጻችሁ ቀን፣ ከተ ሞቻችሁ እንደ ገና መኖሪያ ይሆናሉ:: የፈ ረሱትም እንደ ገና ይታደሳሉ:: [34]በዐላፊ አግዳሚው ዐይን ጠፍ ሆኖ ይታይ የነበ ረው፣ ባድማ መሬት ይታረሳል:: [35]እነር ሱም፣ "ጠፍ የነበረው ይህ ምድር እንደ ዔድን ገነት መሰለ፤ የተደመሰሱ፣ የፈራረሱና ባድማ የሆኑት ከተሞች አሁን መኖሪያና ምሽግ ሆነዋል" ይላሉ:: [36]ከዚያም በዙሪያችሁ የነ በሩ የቀሩት አሕዛብ ፈርሶ የነበረውን መልሼ የሠራሁ፣ ጠፍ የነበረውን ያለመለምሁ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ:: እኔ እግዚአብሔር ተናግሬአለሁ፤ እኔም አደርገ ዋለሁ::"

[37]"ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ 'እንደ ገና ለእስራኤል ቤት ልመና እሺ እላለሁ፤ ይህንም አደርግላቸዋለሁ፤ ሕዝባ ቸውን እንደ በግ መንጋ አበዛዋለሁ፤ [38]በኢ የሩሳሌም በዓላት ላይ እንደሚገኘው የመ ሥዋዕት በግ መንጋ አበዛዋለሁ:: እነሆ! ፈራ ርሰው የነበሩት ከተሞች የብዙ ሕዝብ መኖ ሪያ ይሆናሉ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::' "

36+23 ዘኍ6+27፤ መዝ46+10፤126+2፤ ኢሳ5+16፤37+23፤ ሕዝ20+14፡41፤ 38+23፤39+7፡27-28
36+24ኢሳ43+5-6፤ ሕዝ34+13፤37+21
36+25 ዘሌ14+7፤ 16+14-15፤ዕብ6+21፤ መዝ51+2፡7፤ኢሳ 2+18፤ኢል3+21፤ ዘካ3+4፤13+2፤ሐሥ 22+16፤ዕብ9+13
36+26መዝ51+10፤ ኤር5+3፤24+7፤ሕዝ 18+31፤2ቆሮ3+3
36+27 ኢሳ44+3፤ ኤር 50+20፤ሕዝ 18+21፤ኢል2+29፤ የሐ3+5፤1ተሰ4+8
36+28 ኤር30+22 ፤31+33፤ሕዝ11+17፤ 14+11፤34+24፤37+ 14፡27፤ዘካ8+8
36+29 ሕዝ34+29
36+30 ዘሌ26+4-5፤ ሕዝ34+13-14፤ ሆሴ 2+21-22
36+31 ኢሳ6+5፤ ኤር31+19፤ሕዝ6+9
36+32 ዘዳ9+5፤ ሕዝ16+63
36+33 ዘሌ16+30፤ 26+31፤ኢሳ49+8
36+35 ዘፍ2+8፤ አሞ9+14
36+36ኤር42+10፤ ሕዝ17+22፤37+14፤ 39+27-28
36+37 መዝ102+17፤ ኤር29+12-14፤ዘካ 10+6፤13+9 36+38 ዘፀ6+2፤ 1ነገ8+63፤ 2ዜና 35+7-9

36+22 *ስለ እናንተ ብዬ ሳይሆን፤* እግዚአብሔር ስለ እነርሱ የማይገደው ሆኖ ሳይሆን፣ እርሱ ለእነርሱ የሚያደርግላቸው ማንኛውም ነገር የሚገባቸው ባለመሆኑ ነው (ከዘዳ9+4-6 ጋር ያነ ጻጽሩ)፤ እንዲህ ዐይነቱ ዐረፍተ ነገር፣ ሕዝቅኤል የእውነተኛ ጸጋ ሰባኪ መሆኑን ያረጋግጥለታል:: *ስለ ቅዱስ ስሜ ስል፤* መለኮታዊ ቅጣቱ የዘገየበት ምክንያት፣ በም20 ላይ የተጠቀሰ ቢሆንም (20+9፡14፡22 ይመ)፤ እዚህ ላይ ግን እግዚአብሔር በምሕረቱ ወደ እነርሱ በመመለሱ ምክንያት ነው::

36+23 *አሕዛብ እኔ እግዚአብሔር እንደ ሆንሁ ያውቃሉ፤* እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር ያለው በኪዳን ላይ የተ መሠረተ ኅብረት ዋና ዐላማ፣ መላው ዓለም እውነተኛ አምላክ እርሱ ብቻ እንደሆነ ያውቅ ዘንድ ነው::

36+24 *አስወጣችኋለሁ ... እሰበስባችኋለሁ ... መልሼ አመጣችኋለሁ፤* ሕዝቅኤል፣ የተሐድሶ ተስፋን በተመለከተ በተለ ያዩ አራት ደረጃዎች እንደሚፈጸሙ ከተናገራቸው ትንቢቶች፣ ይህ ዋናውና የመጀመሪያው ሲሆን፣ ይኸውም ከምርኮ ስለ መመለሳቸው ነው::

36+25 *ንጹሕ ውሃ እረጫችኋለሁ፤* በሥርዐቱ መሠረት ለመንጻት በውሃ መረጨት አስፈላጊ ስለመሆኑ ዘፀ30+19-20፤ ዘሌ14+51፤ ዘኍ19+18 ይመ፤ ከዘካ13+1፤ ዕብ10+22 ጋር ያነጻ ጽሩ:: *ከጣዖታቶቻችሁ፤* የ6+4 ማብ ይመ:: *አነጻችኋለሁ፤* ቍ33፤ 37+23፤ ኤር33+8 ይመ::

*36+26-27፤* በ"አዲሱ ኪዳን" ያለውን ሐሳብ ያካተቱ ሐረ ጐችን የያዘ ነው (ኤር31+33-34 ይመ)::

36+26 *አዲስ ልብ፤* የ11+19፤ 18+31 ማብ ይመ:: *አዲስም መንፈስ በውስጣችሁም አሳድራለሁ፤* አእምሮአችሁንና ልባችሁን እለውጣለሁ ማለት ነው:: በዚህና በ11+19 ላይ፣ የሚለውጠውም እግዚአብሔር ራሱ እንደሆነ ተጠቅሶአል:: በ18+31 ላይ (ያንኑ ማብ ይመ) ሊያገኙ ለሚገባቸው ሕዝቡን በጎ ምላሽ እንዲሰጥ ጥሪውን አቅርቦአል:: እግዚአብሔር ለሕዝቡ ያስፈልጋል ብሎ የሚያስበውን ሁሉ ከመስጠት ወደ ኋላ አይልም:: *የሥጋንም ልብ፤* "ሥጋ" የሚለው ቃል በብሉይ ኪዳን ደካማነትንና በቀላሉ ለጕዳት መጋለጥን የሚያመለክት ሲሆን (ኢሳ31+3)፤ በአዲስ ኪዳን ግን በኀጢአት የተሞላውንና እግዚአብሔርን የሚቃወመውን የሰውን ተፈጥሮ ያሳያል (ሮሜ8+5-8 ይመ):: እዚህ ላይ፣ "ከድንጋይ" እንደ ድንጋይ የጠጠረውን ልብ ሳይሆን፣ በተቃራኒው ሊለወጥና ሊመከር የሚችለውን ልብ ያመለክታል::

36+27 *መንፈሴን፤* የሰው መንፈስ የእርሱን ፈቃድ ለማ ድረግ ይችል ዘንድ እግዚአብሔር የራሱን መንፈስ ለሰብአዊ ፍጡር ይሰጣል:: ከቍ25-27 ያለው፣ በመዝ51+7-11 ካለው ጋር ተጓዳኝ ነው::

36+28 *ሕዝቤም ... አምላክ፤* ይህ የኪዳን ቋንቋ ነው (11+20 እና ማብ ይመ)::

36+29 *ከርኵሰታችሁ ሁሉ፤* ከተዘፈቁበት የጣዖት አምልኮና ከሥነ ምግባር ውድቀት ማለት ነው (ቍ25፤ 37+23 ይመ):: *እጠራለሁ፤* እግዚአብሔር በመጀመሪያ ፍጥረቱን በፈጠረ ጊዜ እንዳሰማው ቃል ማለት ነው (ከዘፍ1+5፡8፡10 ጋር ያነጻጽሩ)::

36+30 *በውርደት፤* በቍ15 እንደተጻፈው ማለት ነው::

36+31 *ከዚያም ... ታስታውሳላችሁ፤* ካለመታዘዙ የተነሣ ለሰው ልጅ የማይገባው የእግዚአብሔር ጸጋ ወደ ማስታወስና ወደ ንስሓ ይመራል (ከ6+9፤ 16+63፤ 20+43፤ መዝ130+4 ጋር ያነጻጽሩ)::

36+32 *ለእናንተ ስል ... እንደማላደርግ፤* የቍ22 ማብ ይመ::

36+33 *ቀን፤* ስለመንጻት የተሰጠውን የተስፋ ቃልና (ቍ24-32 እንደ ገና በምድራቸው ላይ እንደሚሰፍሩ የተሰጠውን የተስፋ ቃል (ቍ33-36) ያያይዛል::

36+35 *ዔድን ገነት፤* ልምላሜው በፍጥረት መጀመሪያ ላይ እንደ ነበረው ዐይነት ለም እንደሆነ ተገልጾአል (ከ28+13፤ 31+9 ጋር ያነጻጽሩ):: *ምሽግ ሆነዋል፤* ከ38+11 ጋር ያነጻጽሩ::

36+36 *አሕዛብ ... ያውቃሉ፤* የቍ23 ማብ ይመ::

36+37 *ለእስራኤል ቤት እሺ እላለሁ፤* ከዚህ በፊት እግዚ አብሔር አልቀበልም ያለውን ልመናቸውን እንደ ገና ወደ እርሱ እንዲቀርብ መፍቀዱን ያሳያል (ከ14+3፤ 20+3፡31 ጋር ያነጻ ጽሩ)::

36+38 *እንደሚገኘው የመሥዋዕት በግ መንጋ አበዛዋለሁ፤* ይህ ንጽጽር ተገቢ ስለመሆኑ 1ነገ8+63፤ 1ዜና29+21፤ 2ዜና35+7 ይመ::

## የደረቅ ዐጥንቶች ሸለቆ

**37** *የእግዚአብሔር* እጅ በላዬ ነበረ፤ እርሱም *በእግዚአብሔር* መንፈስ አወጣኝ፤ በሸለቆ መካከልም አኖረኝ፤ ሸለቆውም በዐጥንቶች ተሞልቶ ነበር። [2]በእነርሱም መካከል ወደ ፊትና ወደ ኋላ አመላለሰኝ፤ በሸለቆውም ወለል ላይ በጣም የደረቁ እጅግ ብዙ ዐጥንቶች አየሁ። [3]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ እነዚህ ዐጥንቶች በሕይወት ሊኖሩ ይችላሉን?" ሲል ጠየቀኝ።

እኔም፣ "ጌታ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ ብቻ ታውቃለህ" አልሁ።

[4]ከዚያም እንዲህ አለኝ፤ "ለእነዚህ ዐጥንቶች ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በላቸው፤ 'እናንት ደረቅ ዐጥንቶች፤ *የእግዚአብሔርን* ቃል ስሙ! [5]ጌታ *እግዚአብሔር* ለእነዚህ፤ ዐጥንቶች እንዲህ ይላል፤ "እስትንፋስ* አገባባችኋለሁ፤ እናንተም በሕይወት ትኖራላችሁ። [6]ጅማት አደርግላችኋለሁ፤ ሥጋ አለብሳችኋለሁ፤ በቆዳ እሸፍናችኋለሁ፤ በውስጣችሁም እስትንፋስ አገባባችኋለሁ፤ በሕይወት ትኖራላችሁ፤ እኔም *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ።" '

[7]ስለዚህ እንደ ታዘዝሁት ትንቢት ተናገርሁ፤ ትንቢቱን በምናገርበትም ጊዜ የኰሽኰሽታ ድምፅ ተሰማ፤ ዐጥንቶቹም አንድ ላይ ሆኑ፤ ዐጥንት ከዐጥንት ጋር ተጋጠመ። [8]እኔም ተመለከትሁ፤ ጅማት ነበረባቸው፤ ሥጋም በላያቸው ታየ፤ ቆዳም ሸፍኖአቸዋል፤ እስትንፋስ ግን በውስጣቸው አልነበረም።

[9]ከዚያም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ለነፋሱ ትንቢት ተናገር፤ ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በለው፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ነፋስ ሆይ፤ ከአራቱ ነፋሳት ዘንድ ና፤ በሕይወት እንዲኖሩም በእነዚህ በተገደሉት ላይ እፍ በልባቸው።" ' [10]ስለዚህም እንዳዘዘኝ ትንቢት ተናገርሁ፤ እስትንፋስም ገባባቸው፤ ሕያዋንም ሆኑ፤ እጅግ ታላቅ ሰራዊት ሆነው በእግራቸው ቆሙ።

[11]ከዚያም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ እነዚህ ዐጥንቶች መላው የእስራኤል ቤት ናቸው፤ እንዲህም ይላሉ፤ 'ዐጥንቶቻችን ደርቀዋል፤ ተስፋ የለንም፤ ተቈርጠናል።" [12]ስለዚህ ትንቢት ተናገር እንዲህም በላቸው፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ሕዝቤ ሆይ፤ መቃብሮቻችሁን እከፍታለሁ፤ ከውስጣቸው አወጣችኋለሁ፤ ወደ እስራኤል ምድር መልሼ አመጣችኋለሁ። [13]ከዚያም እናንተ ሕዝቤ ሆይ፤ መቃብሮቻችሁን ከፍቼ ሳወጣችሁ፣ እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ታውቃላችሁ። [14]መንፈሴን በውስጣችሁ አስቀምጣለሁ፤ እናንተም በሕይወት ትኖራላችሁ፤ በገዛ ምድራችሁ አስቀምጣችኋለሁ፤ ከዚያም እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ተናገርሁ፣ እንዳደረግሁትም ታውቃላችሁ፤ ይላል *እግዚአብሔር*።" '

## አንድ ሕዝብ በአንድ ንጉሥ

[15]*የእግዚአብሔር* ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ [16]"የሰው ልጅ ሆይ፤ አንድ በትር ወስደህ፣ 'የይሁዳና የተባባሪዎቹ የእስራኤላውያን' ብለህ ጻፍበት። ከዚያም ሌላ በትር ወስደህ፣ 'የኤፍሬም፣ የዮሴፍና የተባባሪዎቹ የእስራኤል ቤት ሁሉ' ብለህ ጻፍበት። [17]እንደ አንድ በትር ይሆኑ ዘንድ በእጅህ ላይ አጋጥመህ ያዛቸው።

37፥1 ኤር7፥32፤ 8፥2፤ሕዝ1፥3፤ 11፥24፤40፥1፤ ሉቃ4፥1፤ሐሥ8፥39
37፥3 ዘዳ32፥39፤ 1ሳሙ2፥6፤ ኢሳ26፥19፤ 1ቆሮ15፥35
37፥4 ኤር22፥29
37፥5 ዘፍ2፥7፤ መዝ104፥29-30፤ ራእ11፥11
37፥6 ዘፀ6፥2፤ ሕዝ38፥23
37፥9 ቍ14፤ መዝ 104፥30፤ ኢሳ32፥15፤ ኤር49፥36፤ ሕዝ39፥29፤ዳን7፥2፤ 8፥8፤11፥4፤ዘካ2፥6፤ 6፥5፤12፥10፤ራእ7፥1
37፥10 ሕዝ12፥7፤ ራእ11፥11
37፥11 ኢዮ17፥15፤ ሰቆ3፥54
37፥12 ቍ21፤ ዘዳ32፥39፤1ሳሙ2፥6፤ ኢሳ26፥19፤ኤር 29፥14፤ሆሴ13፥14፤ አሞ9፥14-15፤ ሶፎ3፥20፤ዘካ8፥8
37፥13 ዘፀ6፥2፤ ሕዝ17፥24፤ሆሴ13፥14
37፥14 ቍ9፤ ኢሳ11፥2፤ኤር43፥2፤ ሕዝ36፥27-28፡36፤ ኢዩ2፥28-29፤ ራእ11፥11
37፥16 ዘኍ17፥2 -3፤1ነገ12፥20፤ 2ዜና10፥17-19፤ 15፥9
37፥17 ቍ24፤ ኢሳ11፥13፤ ኤር50፥4፤ሆሴ1፥11

*5 በዕብራይስጥ *ነፋስ ወይም መንፈስ ማለትም ነው* (ከቍ6-14 ይመ)

*37፥1-28፤* ሕዝቅኤል ካያቸው ራእዮች አንዱ ክፍል፤ በ1፥2፤ 8፥1፤ 40፥1 ላይ ተጽፎ እንደምናገኘው፣ እዚህ ላይ ጊዜው በውል ተለይቶ ባይገለጽም፣ ነቢዩ ይህን ራእይ ያየው ከ586 ዓ.ቅ.ክ. መሆኑ ግን ግልጽ ነው።

37፥1 *የእግዚአብሔር እጅ፤* የ1፥3 ማብ ይመ። *በእግዚአብሔር መንፈስ፤* ይህን አባባል በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የምናገኘው በ11፥5 ላይ ብቻ ነው። በ8፥3 ላይ እንደተገለጸው፣ "መንፈስ" ማለት ነው። *በሸለቆ፤* በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም በ3፥22-23፤ 8፥4 ላይ፣ "ቈላ" ተብሎ ከተጠቀሰው ጋር ተመሳሳይ ነው። ሕዝቅኤል ቀደም ሲል የእግዚአብሔርን የፍርድ ቃል የተቀበለ ቢሆንም፣ የአሁኑ ግን የተስፋን መልእክት ነው። *ዐጥንቶች፤* በቍ11 ላይ እንደተገለጸው፣ ይህ ትእምርት እስራኤላውያን በምርኮ የነበሩበትን ተስፋ አስቈራጭ ሁኔታ የሚያመለክት ነው።

37፥2 *እጅግ ብዙ ዐጥንቶች፤* በምርኮ የነበረውን ሕዝብ በሙሉ ያመለክታል። *በጣም የደረቁ፤* ከሞቱ ብዙ ጊዜ የሆናቸውን ማለት ነው (1ነገ 17፥17-24፤ 2ነገ4፥18-37 ይመ፤ እንዲሁም 2ነገ13፥21 ይመ)።

37፥4 *ለእነዚህ ዐጥንቶች ትንቢት ተናገር፤* ከዚህ በፊት ሕዝቅኤል ግዑዛን ለሆኑ ፍጥረታት ትንቢት ተናግሮ ነበር (ተራሮች 6፥2፤ 36፥1፤ ደኖች 20፥47) አሁን ደግሞ ሕይወትና እስትንፋስ ለሌላቸው ዐጥንቶች (ቍ9) ትንቢት ተናገረ።

37፥6 *ጅማት ... ሥጋ ... ቆዳ ... እስትንፋስ፤* በአራት መድብ መናገር በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተለመደ ነገር ነው (የ1፥5 ማብ ይመ)።

37፥7 *የኰሽኰሽታ ድምፅ፤* ምናልባት አንዱ ዐጥንት ከሌላው ጋር ሲገናኝ በ3፥12-13 እንደተገለጸው ድምፁ እግዚአብሔር ከመገኘቱ የተነሣ ሊሆን ይችላል።

37፥8 *እስትንፋስ ግን ... አልነበረም፤* ይህ በነቢዩ ራእይ የታየው፣ የእግዚአብሔር ሕዝብ እንደ ገና መፈጠር በዘፍ2፥7 ላይ የተጠቀሰውን የሰውን በሁለት ደረጃ መፈጠር ያስታውሰናል፤ ይኸውም በመጀመሪያ ሰው ከምድር ዐፈር መበጀቱን፤ ከዚያም የሕይወት እስትንፋስን መቀበሉን ነው።

37፥9 *ለነፋሱ፤* የቍጥር 5 አግራጭ ትርጕም ይመ። *አራቱ፤* የ1፥5 ማብ ይመ። *በተገደሉት፤* ሕዝቅኤል የተመለከተው በጦር ሜዳ ተበታትነው የወደቁትን የሰዎች ዐጥንት ነው (ቍ 10 ይመ)።

37፥11 *ዐጥንቶቻችን ... ተቈርጠናል፤* በራእዩ ተስፋ የተሰጠ ቢሆንም፣ ሕዝቡ ያለበት ሁኔታ ግን በከፍተኛ ደረጃ ተስፋ አስቈራጭ ነበር።

37፥12 *መቃብሮቻችሁን፤* ቀደም ሲል የተገለጸው ምስል፣ በጦር ሜዳ ላይ ተበታትነው የወደቁ ዐጥንቶች ሲሆኑ (የቍ9 ማብ ይመ)፤ በዚህ ቍጥር ላይ ግን የተከደነ መቃብር ነው።

37፥14 *በገዛ ምድራችሁ አስቀምጣችኋለሁ፤* እነዚህ ቃላት ግልጽ የሚያደርጉት፣ እግዚአብሔር የተናገረው ስለ ሙታን ትንሣኤ ሳይሆን፣ እስራኤል እንደ ገና በመንግሥትነት እንደምትቋቋም ነው።

37፥16 *አንድ በትር፤* ይህ ሕዝቅኤል በመጨረሻ ትእምርታዊ ተግባሩ የተጠቀመበት ነው (ከ 4፥1፡3፡9፤ 5፥1 ጋር ያነጻጽሩ)። *ጻፍበት፤* በዘካ11፥7 ላይ ያለው ሐሳብ በዚህ ምንባብ ላይ የተመሠረተ ይመስላል።

37፥17 *አጋጥመህ ያዛቸው፤* በትሮቹ በታምር ተገጣጥመዋል ወይም ሕዝቅኤል ራሱ በእጁ ሰብስቦ ይዞአቸው ይሆናል።

18“የአገርህ ልጆች፣ ‘ይህስ ምን ማለትህ እንደ ሆነ አትነግረንምን?’ ብለው ሲጠይቁህ፣ 19እንዲህ በላቸው፤ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ “በኤፍሬም እጅ ያለውን የዮሴፍን በትርና የተባባሪዎቹን የእስራኤላውያንን ነገድ በትር እወስዳለሁ፤ ከይሁዳ በትር ጋር አጋጥሜ አንድ ወጥ በትር አደርጋቸዋለሁ፤ እነርሱም በእጄ አንድ በትር ይሆናሉ።’ ” 20የጻፍህባቸውን በትሮች ከፊት ለፊታቸው ያዝ፤ 21እንዲህም በላቸው፤ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ “እስራኤላውያንን ከሄዱባቸው አሕዛብ መካከል አወጣቸዋለሁ፤ ከየስፍራው ሰብስቤ ወደ ገዛ ምድራቸው እመልሳቸዋለሁ። 22በምድሪቱ በእስራኤል ተራሮች ላይ አንድ ሕዝብ አደርጋቸዋለሁ፤ በሁሉም ላይ አንድ ንጉሥ ይነግሣል፤ ከእንግዲህም ሁለት ሕዝብ አይሆኑም፤ መንግሥታቸውም ከሁለት አይከፈልም። 23በጣዖታቶቻቸው፣ በአስጸያፊ ምስሎቻቸው ወይም በማንኛውም ኀጢአት ራሳቸውን አያረክሱም፤ ነገር ግን እኔን በመተው ከሠሩት ኀጢአት ሁሉ አድናቸዋለሁ፤[a] አነጻቸዋለሁም። እነርሱ ሕዝቤ ይሆናሉ፤ እኔም አምላካቸው እሆናለሁ።”

24“ ‘ባሪያዬ ዳዊት በላያቸው ይነግሣል፤ ሁሉም አንድ እረኛ ይኖራቸዋል፤ ሕጌን ይከተላሉ፤ ሥርዐቴንም በጥንቃቄ ይጠብቃሉ። 25አባቶቻችሁ በኖሩበት፣ ለባሪያዬ ለያዕቆብ በሰጠሁት ምድር ይኖራሉ። በዚያም እነርሱ፣ ልጆቻቸውና የልጅ ልጆቻቸው ለዘላለም ይኖራሉ፤ ባሪያዬ ዳዊትም ለዘላለም ንጉሣቸው ይሆናል። 26ከእነርሱም ጋር የሰላም ቃል ኪዳን አደርጋለሁ፤ ቃል ኪዳኑም የዘላለም ይሆናል። አጸናቸዋለሁ፤ አበዛቸዋለሁ፤ መቅደሴንም በመካከላቸው ለዘላለም አኖራለሁ። 27ማደሪያዬ ከእነርሱ ጋር ይሆናል፤ አምላካቸው እሆናለሁ፤ እነርሱም ሕዝቤ ይሆናሉ። 28መቅደሴም ለዘላለም በመካከላቸው በሚሆንበት ጊዜ፣ አሕዛብ እኔ እግዚአብሔር እስራኤልን እንደ ቀደስሁ ያውቃሉ።’ ”

## በጎግ ላይ የተነገረ ትንቢት

**38** የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ሲል ወደ እኔ መጣ፤ 2“የሰው ልጅ ሆይ፤ ፊትህን በማጎግ ምድር በሚገኘው፣ በሞሳሕና በቶቤል ዋና አለቃ[+] በጎግ ላይ አድርግ፤ በእርሱ ላይ ትንቢት ተናገር፤ 3እንዲህም በል፤ ‘ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ

37፥18 ሕዝ24፥19
37፥19 ዘካ10፥6
37፥21 ቍ12፤ኢሳ 43፥5-6፤ሕዝ20፥42፤ 39፥27፤ሚክ 4፥6
37፥22 ኢሳ11፥13፤ ኤር33፥24፤50፥4፤ ሕዝ17፥22፤34፥13 -14፤ሆሴ1፥11
37፥23 ኤር7፥24፤ ሕዝ11፥18፤36፥28፤ 43፥7፤ናሆ2፥2
37፥24 1ሳሙ13፥14፤መዝ78፥70-71፤ ኢሳ32፥1፤55፥4፤ኤር 30፥21፤ሕዝ21፥27፤ ሆሴ3፥5፤ዘካ 13፥7
37፥25 ዕዝ9፥12፤ መዝ89፥3-4፤ኢሳ 11፥1፤ሕዝ28፥25፤ 34፥23-24፤አሞ9፥15
37፥26 ዘፍ9፥16፤ ዘሌ26፥11፤ዘኍ25፥12፤ዘዳ29፥14፤ኤር 30፥19፤ሕዝ16፥62፤ ዕብ13፥20
37፥27 ዘሌ26፥11፤ ሕዝ34፥30፤36፥28፤ 2ቆሮ6፥16
37፥28 ዘፀ31፥13፤ ሕዝ43፥9፤ሆሴ1፥10 -11፤ሶፎ3፥15
38፥2 ቍ14፤ ዘፍ10፥2፤ሕዝ27፥13፤ 39፥11
38፥3 ሕዝ39፥1

[a]23 በብዙ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆችም እንዲሁ (በተጨማሪ ሰብዓ ሊቃናት ይመ) ሲሆን፣ አብዛኞዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ግን *ኀጢአት የሠሩባቸውን የመኖሪያ ስፍራዎቻቸውን ሁሉ* ይላሉ
[+]2 ወይም *የሮሽ አለቃ*

37፥18 *አትነግረንምን?* የሕዝቅኤል ትእምርታዊ ተግባር፣ የሕዝቡን ስሜት በሚገባ አነሳስቶአል (12፥9፤ 21፥7፤ 24፥19 ይመ)።

37፥19 *በእጄ አንድ በትር ይሆናሉ፤* ከንጉሥ ሰሎሞን ሞት በኋላ ለሁለት ተከፍሎ የነበረው መንግሥት አንድ እንደሚሆን፣ ሕዝቅኤል በተጠቀመበት ትእምርታዊ ተግባር እግዚአብሔርም ተናገረ (1ነገ12 ይመ)። ተከፋፍለው የነበሩት ሁለቱ የእስራኤል መንግሥታት አንድ እንደሚሆኑ እስራኤል ተመልሳ አንድ እንደምትሆን ስለተነገሩት ተመሳሳይ ትንቢቶች 33፥23፡29፤ ኤር3፥18፤ 23፥5-6፤ ሆሴ1፥11፤ አሞ9፥11 ይመ።

37፥22 *በእስራኤል ተራሮች፤* 6፥2-3፤ 34፥13፤ 36፥1 ይመ። *አንድ ንጉሥ፤* “ንጉሥ” የሚለው ቃል ወደፊት የሚመጣውን ገዥ ለማመልከት የተጠቀሰው፣ እዚህ ላይና ቍ24 ላይ ብቻ ነው፤ ቍ24 ይመ (የ34፥24 ማብ ይመ)፤ 7፥27 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 44፥3፤ 45፥7-9 እና ይኸው ሐሳብ በተደጋጋሚ የተገለጹበትን ምዕራፎች (45-48) ይመ።

37፥23 *በጣዖታታቸው፤* ከጥንት የቈየና እግዚአብሔርን ዋነኛ በደል ነው (የ6፥4 ማብ ይመ)። እኔን *በመተው፤* ከኤር 2፥19፤ 3፥22 ጋር ያነጻጽሩ። *አነጻቸዋለሁ፤* ተመሳሳይ ሐሳብ ከተሰጠበት ከ36፥25 ጋር ያነጻጽሩ። *ሕዝቤ ... አምላካቸው፤* የ11፥20 ማብ ይመ።

37፥24 *ባሪያዬ ዳዊት፤* በ34፥23 እንደተገለጸው የሚመጣው መሲሐዊው ገዥ ዳዊት ተብሎአል፤ ይህም ከዳዊት ዘር በመሆኑና ዳዊት ለእስራኤል ያደረገው ሁሉ፣ እንዲያውም ከዚያ በላይ ስለሚፈጽም ነው። *ይነግሣል፤* የቍ22 ማብ ይመ። *እረኛ፤* በ34፥23 እንደ ተገለጸው የሚመጣው ገዥ መንጋውን በሚጠብቅ እረኛ ተመስሎአል (ከዮሐ10 በተለይም ከቍ16 ጋር ያነጻጽሩ)።

37፥25 *ለባሪያዬ ለያዕቆብ፤* 28፥25 እና ማብ ይመ።

37፥26 *የሰላም ቃል ኪዳን፤* 34፥25 እና ማብ ይመ። *ቃል ኪዳኑም ለዘላለም፤* 16፥60 እና ማብ ይመ። ይህ ሐረግ በብሉይ ኪዳን 16 ጊዜ ተጠቅሶአል፤ ይህም በኖኅ ቃል ኪዳን ጊዜ (ዘፍ9፥16)፣ በአብርሃም (ዘፍ17፥7፡13፡19)፣ በዳዊትና (2ሳሙ 23፥5)፣ በአዲሱ ኪዳን (ኤር32፥40) ነው፤ ይህን ከፊንሐስ ቃል ኪዳን ጋር ያነጻጽሩ (ዘኍ25፥12-13)። *መቅደሴንም በመካከላቸው ... አኖራለሁ፤* እግዚአብሔር ከዚህ ቀደም እንዳደረገው ማለት ነው። የወደፊቱን ዘመን በተመለከተ ሕዝቅኤል ባየው ራእይ እንደተገለጸው፣ እንደገና የሚታነጸው ቤተ መቅደስ የሚገኘውም በእስራኤል ሕዝብ መካከል ነው (ም40-48)፤ ቍ27-28 ይመ።

*38፥1፤* ይህ ዐረፍተ ነገር ራሱን የቻለ አንድ ክፍል በሆነው በም38-39 ውስጥ፣ በተደጋጋሚ የመግቢያ ሐሳብ ሆኖ ይገኛል። በዳዊት ቤት መሪነት (ም37) ወደ ፊት የእስራኤል መንግሥት ሲመሠረት፣ የዓለም መንግሥታት ተባብረው የእግዚአብሔርን መንግሥት ለማጥፋት እንዲነሡ ያደርጋቸዋል። በኢየሩሳሌም ላይ የሚዘምትበት ቍጥር ስፍር የሌለው ሰራዊት ሬሳ በተስፋዪቱ ምድር ላይ ይወድቃል፤ የፖሌስቲና ምድርም የጠላት ሰራዊት ሬሳ መቀበሪያ ትሆናለች (ከም37 ጋር ያነጻጽሩ)።

38፥2 *የሰው ልጅ ሆይ፤* የ2፥1 ማብ ይመ። *ፊትህን ... አድርግ፤* የ20፥46 ማብ ይመ። *በማጎግ ምድር፤* በዘፍ10፥2፤ 1ዜና1፥5 ላይ እንደተገለጸው ማጎግ ከያፌት ልጆች አንዱ በመሆኑ፣ የሕዝቡም ስም መጠሪያ ይኸው ነው። በሕዝ39፥6 ላይም አንድን ሕዝብ የሚያመለክት ነው። የዚህ ስም መነሻ ሆኖ የሆነው “ማ” በዕብራይስጥ “የ... ቦታ” ማለት ነው፤ ስለዚህም ማጎግ የሚለው ቃል “የጎግ ምድር” ማለት ሊሆን ይችላል። እስራኤላውያን ቀደም ሲል ከካም ልጆችና ከሌሎች የሴም ሕዝቦች ጥቃት ደርሶባቸዋል። እዚህ ላይ የተገለጸው፣ የወደፊቱ የጠላትነት ትብብር በያፌት ዘሮች የሚመራና እነርሱንም የሚያካትት መሆኑን ነው (ከዘፍ10 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሞሳህና ቶቤል፤* እነዚህ የያፌት ልጆች ሲሆኑ (ዘፍ10፥2፤ 1ዜና1፥5፣ ከትንሿ እስያ በስተ ምስራቅ የሚገኙም ናቸው ከ27፥13፤ 32፥26 ጋር ያነጻጽሩ)። እነዚህም፣ ከእስራኤል በስተ ሰሜን የሚገኙ አገሮችና ሕዝቦች ናቸው (ከቍ6፡15፤ 39፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። በአሦራውያንና በባቢሎናውያን ዘመን እንደ ሆነው ሁሉ፣ በአብዛኛው ወራሪ የሚመጣው ከሰሜን ነበር። *ዋና አለቃ፤* ይህም የሚያመለክተው የጦር ሰራዊቱን ጠቅላይ አዛዥ ነው፤ በአማራጭ ትርጕሙ ላይ፣ “የሮሽ አለቃ” እንደሆነ ተጠቅሶአል፤ ይህ ትክክል ከሆነ፣ “ሮሽ” ያልታወቀ ሕዝብ ወይም ስፍራ ነው። ይህን ስም ከሩሲያ ጋር ማዛመዱ የማይሆን ነገርና ማስረጃ የማይገኝለት ነው። *ጎግ፤* ስሙ በራእ20፥8 እና እዚህ ላይ ብቻ የተጠቀሰ ንጉሥ ወይም መሪ ነው። ይህን ስም ከብዙ ሰዎች ጋር ለማቈራኘት ተሞክሮአል፤ ከነዚህም መካከል፤ የሊድያ ንጉሥ ጊገስ (660 ዓ.ቅ.ክ.) ይሆናል ተብሎም ነበር። ምናልባትም ስሙ እንዲታወቅ አለመደረጉ፣ ሆን ተብሎም ሊሆን ይችላል፤ ምክንያቱም ወደ ፊት የሚነሣውን የእግዚአብሔርን ሕዝብ ጠላት ሊወክል የሚችል ነው።

ይላል፤ "የሞሳሕና የቶቤል ዋና አለቃ* ጎግ ሆይ፤ ተነሥቼብሃለሁ:: [4]ወደ ኋላ እመልስሃለሁ፤ መንጋጋህ ውስጥ መንጠቆ አስገብቼ ከመላው ሰራዊትህ ጋር፣ ፈረሶችህን፣ ፈረሰኞችህን ከነሙሉ ትጥቃቸው፣ ትልቅና ትንሽ ሰይፍ የያዙትን ሁሉ፣ ሰይፋቸውንም የወለወሉትን ሁሉ አስወጣለሁ:: [5]ጋሻ የያዙና የራስ ቍር የደፉት ሁሉ፣ ፋርስ፣ ኢትዮጵያና ፉጥ ከእነርሱ ጋር ይሆናሉ:: [6]ደግሞም ጎሜርን ከወታደሮቹ ጋር፣ ራቅ ካለው ሰሜንም የቴርጋማን ቤት ከወታደሮቹ ሁሉ ጋር ብዙ ሕዝቦችን ከአንተ ጋር አስወጣለሁ::"

[7]" 'አንተና በዙሪያህ የተሰበሰቡት ሁሉ ተነሡ፤ ተዘጋጁ፤ አንተም መሪያቸው ሁን:: [8]ከብዙ ቀን በኋላ ለጦርነት ትጠራለህ:: በኋለኛው ዘመንም ከጦርነት ያገገመችውን፣ ሕዝቧ ከአያሌ አሕዛብ መካከል ወጥቶ የተሰበሰበውን፣ ለብዙ ጊዜ ባድማ በነበረው በእስራኤል ተራሮች ላይ የሰፈረውን ወገን ትወራለህ:: ከሕዝቦች መካከል ወጥተው፣ አሁን ሁሉም በሰላም ይኖራሉ:: [9]አንተና ወታደሮችህ ሁሉ፣ ከአንተም ጋር ያሉት ብዙ ሕዝቦች እንደ ማዕበል ትወጣላችሁ፤ ምድርን እንደሚሸፍን ደመናም ትሆናላችሁ::

[10]" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "በዚያ ቀን ሐሳብ ወደ አእምሮህ ይመጣል፤ ክፉትንም ታውጠነጥናለህ::" [11]እንዲህም ትላለህ፤ "ቅጥር የሌላቸውን መንደሮች ምድር እወራለሁ፤ ሁሉም ያለ ቅጥር፣ ያለ በርና ያለ ብረት መወርወሪያ የሚኖረውን፣ ሰላማዊና ያለ ሥጋት የተቀመጠውን ሕዝብ እወጋለሁ፤ [12]እዘርፋለሁ፤ እነጥቃለሁ፤ እንዲሁም ከአሕዛብ ተሰባስቦ እንደ ገና በሰፈረው፣ በከብትና በሸቀጥ በከበረው፣ በምድሪቱም መካከል በሚኖረው ሕዝብ ላይ እጄን አነሣለሁ::" [13]ሳባና ድዳን፣ የተርሴስ ነጋዴዎችና መንደሮቿም ሁሉ† እንዲህ ይሉሃል፤ "ልትዘርፍ መጣህን? ሰራዊትህን ያሰባሰብኸው ለመበዝበዝ፣ ወርቅና ብሩን አጋብሶ ለመሄድ፣ ከብቱንና ሸቀጡን ለመውሰድ፣ ብዙ ምርኮ ይዞ ለመመለስ ነውን?" '

[14]"ስለዚህ የሰው ልጅ ሆይ፤ ትንቢት ተናገር፤ ጎግንም እንዲህ በለው፤ 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "በዚያ ቀን ሕዝቤ እስራኤል በሰላም መቀመጡን ዐውቀህ አትንቀሳቀስምን? [15]በስተ ሰሜን ርቆ ከሚገኘው ቦታ ትመጣለህ፤ አንተና ከአንተም ጋር ብዙ ሕዝቦች፣ እጅግ ታላቅ ኀያል ሰራዊትም በፈረሶች ላይ ሆናችሁ ትመጣላችሁ:: [16]ምድርን እንደሚሸፍን ደመና ሆነህ በሕዝቤ በእስራኤል ላይ ትወጣለህ:: ጎግ ሆይ፤ በፊታቸው ቅድስናዬን ስገልጥ ሕዝቦች እኔን ያውቁ ዘንድ በኋለኛው ዘመን በምድሬ ላይ አመጣሃለሁ::"

[17]" 'ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "በቀደመው ዘመን በባሪያዎቼ በእስራኤል ነቢያት ስለ እርሱ የተናገርሁለት ያ ሰው አንተ አይደለህምን? በዚያን ወቅት አንተን በእነርሱ ላይ እንደማመጣባቸው ለብዙ ዓመታት ትንቢት ተናገሩ::" [18]በዚያን ጊዜ እንዲህ ይሆናል፤ "ጎግ የእስራኤልን ምድር ሲወጋ፣ ብርቱ ቍጣዬ ይነሣሣል፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር:: [19]በቅናቴና በሚያስፈራው ቍጣዬ በእስራኤል ታላቅ የምድር መንቀጥቀጥ ይሆናል ብዬ

38+4 2ነገ19+28፤ ኢሳ43+17፤ሕዝ29+4፤ 139+2፤ዳን11+40
38+5 ዘፍ10+6፤ ሕዝ27+10
38+6 ዘፍ10+2:3፤ ሕዝ32+30
38+7 ኢሳ8+9
38+8 ቍ14፤ኢሳ 11+11፤24+22፤ኤር 23+6፤ሕዝ28+26፤ ኢል3+1
38+9 ቍ16፤ኢሳ 25+4፤28+2፤ኤር 4+13፤ኢል2+2፤ ራእ20+8
38+10 መዝ36+4፤ ኤር17+10፤ሚክ2+1
38+11 ዘፍ34+25፤ ኤር49+31፤ዘካ2+4
38+13 ዘፍ10+4:7፤ 25+3፤ኢሳ10+6፤ 33+23፤ኤር15+13
38+14 ቍ8፤ዘሌ 25+18፤ኤር16+15፤ ዘካ 2+5
38+15 ሕዝ32+30፤ 39+2፤ራእ20+8
38+16 ቍ9፤ ዘሌ10+3፤ኢሳ29+23፤ ሕዝ39+21፤ ኢል3+11
38+19 መዝ18+7፤ ኢሳ24+18፤ሕዝ 5+13፤ኢል2+10፤ 3+16፤ሐጌ2+6:21፤ ራእ6+12

*3 ወይም *የሮሽ አለቃ ጎግ*
†13 ወይም *ጠንካራ መንደሮችዋ*

38+3 *ተነሥቼብሃለሁ፤* የ5+8 ማብ ይመ::

38+4 *ወደ ኋላ እመልስሃለሁ፤* የሚመጣውን ነገር ሁሉ እግዚአብሔር ሙሉ በሙሉ የሚቈጣጠር መሆኑን በአጽንኦት ያሳያል:: *መንጋጋህ ውስጥ መንጠቆ አስገብቼ፤* በ29+4 ላይ እንደ ተገለጸው እግዚአብሔርም ጎግንም እንደ ፈሪያን ሁሉ፣ ልክ እንደ እንስሳ ለጉሞ ወደፈለገው አቅጣጫ ይመራዋል ማለት ነው::

38+5 *ኢትዮጵያ፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ:: ከሰሜን የሚመጡት ወራሪ ኀይሎች (ቍ2 እና ማብ ይመ) ከደቡብ ከሚመጡት ሰራዊቶች ጋር አንድ ይሆናሉ:: *ፉጥ፤* በአፍሪካ የምትገኘው ሊቢያ ናት::

38+6 *ጎሜር፤* በስተሰሜን የሚገኝ የጎግ ተባባሪ ነው (የቍ2 ማብ ይመ)፤ ይህም በዘፍ10+3 እና በ1ዜና1+6 ላይ እንደተገለጸውም ከያፌት ልጆች አንዱ ነው:: ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጪ በተገኙት መረጃዎች መሠረት፣ እነዚህ ሕዝቦች የመጡት ከጥቁር ባሕር በስተ ሰሜን በኩል ነው:: *ቴጋርማን ቤት፤* የ27+14 ማብ ይመ:: በዘፍ10+3፤ 1ዜና1+6 መሠረት፣ ቴጋርማን ከጎሜር ልጆች አንዱ ነው::

38+8 *ከብዙ ቀን በኋላ ... በኋለኛው ዘመንም፤* ከም34-37 እንደተገለጸው፣ የእስራኤል ሕዝብ ከተሰደደበት ተመልሶ በራሱ ምድር እንደገና የሚሰፍርበትንና ብሔራዊ አንድነቱን የሚያረጋግጥበትን ሁኔታ ያመለክታል::

38+9 *እንደሚሸፍን ደመና፤* ወራሪ ኀይል ልክ እንደዚሁ ከሰሜን እንደሚመጣ ኤርምያስም ተናግሮአል (ኤር4 13)::

38+10 *በዚያ ቀን፤* በሌሎች የትንቢት መጻሕፍት የተለመደ ሐረግ ቢሆንም፣ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የሚገኘው እዚህ ላይ ብቻ ነው፤ ይህም ጎግ እስራኤልን የሚወርበትን ቀን ያመለክታል:: *ሐሳብ ወደ አእምሮህ ይመጣል፤* በመጽሐፍ ቅዱስ አብዛኛውን ጊዜ እንደታየው፣ ሰው ለሚያከናውነው ተግባር (ከዘዳ31+3፤ ኢሳ10+6-7 ጋር ያነጻጽሩ) መነሥኤው መለኮት ነው (ቍ4):: *ክፉትንም ታውጠነጥናለህ፤* የወረራውን ዘመቻ የሚያመለክት ነው (ቍ12 ይመ)::

38+11 *ቅጥር የሌላቸውን መንደሮች ምድር፤* ፍጹም ደስታና ሰላም የሰፈነበትን መጪውን ጊዜና መከላከያ ግንብ ወይም ምሽግ ምንም ግድግዳ የማያስፈልግበትን ዘመን ያመለክታል:: በዘካ2+4-5 እንደተጠቀሰውና በዚህም ምንባብ እንደተገለጸው አስተማማኙ ጠባቂ እግዚአብሔር ብቻ ነው (ከ36+35-36 ጋር ያነጻጽሩ)::

38+12 *በምድሪቱም መካከል፤* በዕብራይስጥ፣ "መካከል" የሚለው ቃል "እምብርት" ማለትም ነው፤ ሥዕላዊ በሆነ አገላለጽ እግዚአብሔር ከዓለም ጋር ላለው ግንኙነት እስራኤል አስፈላጊ መሆንዋን ያመለክታል (ይህ ሐሳብ በ5+5 ላይም ይገኛል):: ይህ ቃል በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በሌላ ስፍራ የሚገኘው በመሳ9+37 ላይ ብቻ ነው:: በዕብራይስጥ፣ "ምድር" የሚለው ቃል፣ "መሬት" ማለትም ነው፤ በሥነመለኮታዊ አገላለጽ፣ ኢየሩሳሌም የእስራኤል ምድርም ማዕከል ብቻ ሳትሆን፣ በአጠቃላይ የመሬትም ማእከል ናት::

38+13 *ሳባ፤* በዓረብ ልሳነ ምድር በስተደቡብ ምዕራብ የምትገኝና በንግድ የታወቀች አገር ስትሆን፣ እርሷም የዛሬዪቱ የመን ናት (ኢዮ6+19፤ 23+42፤ 27+22፤ 1ነገ10+1-2 ይመ):: *ድዳን፤* የ25+13 ማብ ይመ:: ተርሴስ፤ የ27+12 ማብ ይመ::

38+17 *ስለ እርሱ የተናገርሁለት ያ ሰው አንተ አይደለህምን?* ምናልባት በእግዚአብሔርና በሕዝቡ ላይ በተነሡት ጠላቶች ላይ ቀደም ሲል የተነገሩትን የፍርድ ትንቢቶች በአጠቃላይ የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም::

38+19 *የምድር መንቀጥቀጥ፤* ምድሩን ለመውረር የመጣውን ኀይለኛ ሰራዊት ለማሸበር የሚመጣውን የህልዎተ እግዚአብሔርን ኀያልነት የሚያመለክት ነው::

ተናግሬአለሁ:: [20]የባሕር ዓሦች፣ የሰማይ ወፎች፣ የምድር አራዊት፣ በምድር ላይ የሚሳብ ማንኛውም ፍጡር፣ እንዲሁም በምድር ላይ የሚኖሩ ሰዎች ሁሉ፣ በፊቴ ይንቀጠቀጣሉ፤ ተራሮች ይገለባበጣሉ፤ ገደሎች ይናዳሉ፤ [21]በተራሮቼም ሁሉ በጎግ ላይ ሰይፍ እጠራለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ የእያንዳንዱም ሰው ሰይፍ በወንድሙ ላይ ያርፋል:: [22]በቸነፈርና በደም መፋሰስ እፈርድበታለሁ፤ የዝናብ ዶፍ፣ የበረዶ ድንጋይ፣ የሚያቃጥል ድኝ፣ በእርሱና በወታደሮቹ፣ ከእርሱም ጋር ባሉት ሕዝቦች ላይ አወርዳለሁ:: [23]በዚህም ታላቅነቴንና ቅድስናዬን አሳያለሁ፤ በብዙ ሕዝቦች ፊት ራሴን አሳውቃለሁ፤ ከዚያም እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::" '

**39** "አንተ የሰው ልጅ ሆይ፤ በጎግ ላይ ትንቢት ተናገር፤ እንዲህም በል፤ 'ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "የሞሳሕና የቶቤል ዋና አለቃ[ሀ] ጎግ ሆይ፤ ተነሥቼብሃለሁ፤ [2]ወደ ኋላ እመልስሃለሁ፤ እንዲሁም እጐትትሃለሁ፤ ከሩቅ ሰሜን አምጥቼ በእስራኤል ተራሮች ላይ እሰድሃለሁ:: [3]በግራ እጅህ ያለውን ቀስትህን እመታለሁ፤ በቀኝ እጅህ የያዝሃቸውንም ፍላጾች አስረግፍሃለሁ:: [4]አንተና ወታደሮችህ ሁሉ፣ ከአንተም ጋር ያሉ ሕዝቦች በእስራኤል ተራሮች ላይ ትወድቃላችሁ:: ነጣቂ አሞሮችና የዱር አራዊት ይበሏችሁ ዘንድ አሳልፌ እሰጣችኋለሁ:: [5]አውላላ ሜዳ ላይ ትወድቃለህ፤ እኔ ተናግሬአለሁና፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*:: [6]በማጎግና ያለ ሥጋት በባሕር ዳርቻ በሚኖሩት ላይ እሳት እሰዳለሁ፤ እነርሱም እኔ *እግዚአብሔር* እንደ ሆንሁ ያውቃሉ::"

[7]" 'ቅዱሱ ስሜ በሕዝቤ በእስራኤል ዘንድ እንዲታወቅ አደርጋለሁ፤ ከእንግዲህ ወዲያ ቅዱስ ስሜ እንዲናቅ፣ እንዲቃለል አልፈልግም፤ አሕዛብም እኔ *እግዚአብሔር* የእስራኤል ቅዱስ እንደ ሆንሁ ያውቃሉ:: [8]እነሆ ይመጣል፤ በእርግጥም ይሆናል፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*፤ ያ ያልሁት ቀን ይህ ነው::

[9]" 'ከዚያም በእስራኤል ከተሞች የሚኖሩ ሁሉ ወጥተው የጦር መሣሪያውን፣ ትልል ቁንና ትንንሹን ጋሻ፣ ቀስቱን፣ ፍላጻውን፣ የጦር ዱላውንና ጦሩን ሰብስበው ማገዶ በማድረግ ያነዱታል፤ ሰባት ዓመት ይማግዱታል:: [10]ከሜዳ ላይ ዕንጨት መልቀም፣ ከዱርም ዛፍ መቍረጥ አያስፈልጋቸውም፤ የጦር መሣሪያቸውን በመማገድ ይጠቀማሉና:: የዘረፏቸውን ይዘርፋሉ፤ የበዘበዟቸውን ይበዝብዛሉ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::

[11]" 'በዚያ ቀን ሰዎች በምሥራቅ በኩል ወደ ባሕሩ[ለ] በሚጓዙበት ሸለቆ፣ ለጎግ የመቃብር ስፍራ በእስራኤል እሰጠዋለሁ:: ጎግና ሰራዊቱ ሁሉ በዚያ ስለሚቀበሩ፣ የተጓዦችን መንገድ ይዘጋሉ፤ ስለዚህም የሐሞን ጎግ[ሐ] ሸለቆ ይባላል::

[12]" 'ምድሪቱን ለማጽዳት፣ የእስራኤል ቤት ሰዎች ሰባት ወር ሙሉ ይቀብሯቸዋል:: [13]የምድሪቱ ሰዎች ሁሉ ይቀብሯቸዋል፤ እኔ የምከብርበትም ዕለት የመታሰቢያ ቀን ይሆናቸዋል፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::

[14]" 'ሰዎች ምድሪቱን ለማጽዳት በየጊዜው ይቀጠራሉ:: አንዳንዶቹ ምድሪቱን ያስሳሉ፤ ከእነርሱም በተጨማሪ ሌሎች ሳይቀበሩ የቀሩትን ይቀብራሉ:: ከሰባት ወር በኋላም ፍለጋ ይጀምራሉ:: [15]እነርሱም በምድሪቱ መካከል ሲሄዱ፣ ከእነርሱ አንዱ የሰው ዐፅም ባየ ቍጥር ምልክት ያደርግበታል፤ ይህም መቃብር ቈፋሪዎች በሐሞን ጎግ ሸለቆ እስኪቀብሩት ድረስ ነው:: [16]በዚያም ሐሞና[መ] የምትባል ከተማ አለች፤ ስለዚህ ምድሯን ያጸዳሉ::'

38+20 ዘፀ15+14፤ ኢዮ14+18፤መዝ 76+8፤ኢሳ42+15፤ ሆሴ4+3፤ናሆ1+5
38+21 1ሳሙ14+20፤2ዜና20+23፤ኢሳ 66+16፤ኤር25+29፤ ሐጌ2+22
38+22 ዘፍ19+24፤ ዘፀ9+18፤መዝ18+12 ፤ኢሳ66+16፤ኤር25+31፤ሕዝ13+11፤ 14+19፤28+23፤36+5፤ራእ9+17፤16+21
38+23 ሕዝ20+42፤ 36+23፤37+6
39+1 ዘፍ10+2፤ ሕዝ27+13፤38+2:3
39+2 ሕዝ32+30፤ 38+4:15
39+3 መዝ76+3፤ ሆሴ1+5፤አሞ2+15
39+4 ቍ17-20፤ ዘፍ40+19፤ኤር25+33፤ሕዝ29+5፤33+27
39+5 ሕዝ32+4
39+6 ዘፍ10+2፤ዘፀ 6+7፤ኤር25+22፤ሕዝ 30+8፤ራእ20+9
39+7 ዘፀ20+7፤ኢሳ 12+6፤49+26፤54+5፤ ሕዝ13+19፤20+9፤ 36+23
39+8 ሕዝ7+6
39+9 መዝ46+9፤ 76+3
39+10 ዘፀ3+22፤ ኢሳ14+2፤33+1፤ ዕን2+8
39+11 ኢሳ34+3፤ ሕዝ38+2
39+12 ዘዳ21+23
39+13 ሕዝ28+22

[ሀ]1 *ወይም የሮሽ አለቃ ጎግ*
[ለ]11 *የሙት ባሕርን ያመለክታል*
[ሐ]11 *ሐሞንጎግ ማለት የጎግ መንጋ ማለት ነው*
[መ]16 *ሐሞና ማለት መንጋ ማለት ነው*

*38+20፤* የእንስሳትን ዓለም በአራት ክፍሉ መናገር፣ የተፈጥሮን ሙሉነት ያመለክታል (የ1+5 ማብ ይመ፤ ከዘፍ 9+2፤ 1ነገ4+33፤ ኢዮ12+7-8 ጋር ያነጻጽሩ)::

38+21 *ሰይፍ እጠራለሁ፤* የእግዚአብሔርን የፍርድ ሰይፍ ማለት ነው (ኢሳ34+5-6፤ ኤር25+29):: *የእያንዳንዱም ሰው ሰይፍ በወንድሙ ላይ ያርፋል፤* በኢዮሳፍጥ ዘመነ መንግሥት (2ዜና20+22-23) ይሁዳን በወጋው ሰራዊት ላይ እንደ ሆነው ሁሉ፣ እስራኤልን ለመውጋት የተባበሩት ጠላቶቿ ሁሉ፣ በራሳቸው ላይ ሰይፍን ይመዝዛሉ::

*38+22፤* የተዘረዘሩት መለኮታዊ የጦር መሣሪያዎች፣ እግዚአብሔር ያለ ምንም ምድራዊ ሰራዊት ራሱ በቀጥታ በጉዳዩ እንደሚገባ ያመለክታል::

39+1 *የሞሳሕ ... ዋና አለቃ፣ ጎግ፤* የ38+2 ማብ ይመ:: ከቍ1-16 ያለው አዲስ ዝርዝሮችን ጨምሮአል፤ እነዚህም በም 38 ላይ ከተገለጹት ዋና ዋና ሁኔታዎች ጋር ተመሳሳይ ናቸው::

39+2 *ከሩቅ ሰሜን፤* በ38+6:15 እንደተገለጸው ማለት ነው::

39+3 *ቀስትህን፤* ከኤር6+23 ጋር ያነጻጽሩ:: የእስራኤል ጠላቶች ፍላጻቻቸውን፤ ከመወርወራቸው በፊት መሣሪያቸውን ይነጥቃቸዋል::

39+4 *ነጣቂ አሞሮች ... ይበሏችሁ ዘንድ፤* ከቍ17-20 ድረስ በሰፋት የተጠቀሰ ዐቢይ ሐሳብ ነው::

39+6 *እሳት እሰዳለሁ፤* 30+8 እና ማብ ይመ::

39+9 *ያነዱታል፤* እግዚአብሔር እንደሚያቃጥላቸው በመዝ46+9 ላይ ከተጠቀሰው ጋር ያነጻጽሩ:: *ሰባት፤* በእግዚአብሔር ሕዝብ ላይ የታወጀውን ታላቅ ጦርነት ፍጻሜና የወራሪውን ጠላት ሰራዊት የቱን ያህል ብዛት እንዳለው የሚያመለክት ትእምርታዊ ቍጥር ነው::

39+11 *በኩል፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ወደ ምሥራቅ አቅጣጫ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ዘፍ2+14፤ 4+16፤ 1ሳሙ13+5 ይመ)::

39+12 *ምድሪቱን ለማጽዳት፤* በሥርዐቱ መሠረት መንጻት በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ዐቢይ ሥነ መለኮታዊ ጽንሰ ሐሳብ ነው (22+26፤ 24+13፤ 36+25:33፤ 37+23 ይመ):: በተለይ አስከሬኖች በሥርዐቱ ያልነጹ ናቸው (ዘሌ5+2፤ 21+1:11፤ 22+4፤ ዘኍ5+2፤ 6+6-12፤ 19+16፤ 31+19 ይመ)::

39+13 *የምድሪቱ ሰዎች፤* በዚህ ክፍል ተለይቶ የተገለጸ የኅብረተ ሰብ ክፍል ባይኖርም፣ 7+27 እና ማብ ይመ::

39+14 *ሰዎች ... በየጊዜው ይቀጠራሉ፤* ሕዝቡ ሰባት ወር ሙሉ ሙታናቸውን ከቀበሩ በኋላ፣ አንድ ዐጥንት እንኳ ሳይቀበር እንዳይቀር የተመረጡ ሰዎች ምድሪቱን ሙሉ በሙሉ በማንጻት ሥራ ላይ ይሰማራሉ፤ ይህ የሚሆንበት ምክንያት፣ በሥርዐቱ መሠረት መንጻት ዋና ዐላማቸው ስለ ሆነ ነው::

39+15 *ምልክት፤* ምናልባት አንድ ትልቅ ድንጋይ ወይም የትናንሽ ድንጋዮች ክምር ሊሆን ይችላል::

[17]“ ‘የሰው ልጅ ሆይ፤ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ‘ማንኛውንም ዐይነት ወፍና የዱር አራዊት ሁሉ ጥራ፤ እንዲህም በላቸው፤ “ከየአቅጣጫው ተሰብስባችሁ እኔ ወደማዘጋጅላችሁ መሥዋዕት ኑ፤ ይህም በእስራኤል ተራሮች ላይ የሚሆን ታላቁ መሥዋዕት ነው:: በዚያ ሥጋ ትበላላችሁ፤ ደምም ትጠጣላችሁ:: [18]እንደ አውራ በግና እንደ ጠቦት፤ እንደ ፍየልና እንደ ወይፈን፣ የኀያላን ሰዎችን ሥጋ ትበላላችሁ፤ የምድርንም መሳፍንት ደም ትጠጣላችሁ፤ እነዚህ ሁሉ የሰቡ የባሳን ከብቶች ናቸው:: [19]እኔ በማዘጋጅላችሁም መሥዋዕት እስክትጠግቡ ስብ ትበላላችሁ፤ እስክትሰክሩም ደም ትጠጣላችሁ:: [20]በገበታዬም ፈረሶችንና ፈረሰኞችን፣ ኀያላን ሰዎችንና ከየወገኑ የሆኑትን ወታደሮች እስክትጠግቡ ትበላላችሁ፤” ይላል ጌታ እግዚአብሔር::’

[21]“ክብሬን በአሕዛብ መካከል እገልጣለሁ፤ አሕዛብም ሁሉ በእነርሱ ላይ ያመጣሁትን ቅጣትና በላያቸው ላይ የጫንሁትን እጅ ያያሉ:: [22]ከዚያን ጊዜ ጀምሮ የእስራኤል ቤት እኔ እግዚአብሔር፣ አምላካቸው እንደ ሆንሁ ያውቃሉ:: [23]አሕዛብም የእስራኤል ሕዝብ ለእኔ ታማኞች ባለመሆን ከሠሩት ኀጢአት የተነሣ እንደ ተሰደዱ ያውቃሉ፤ ስለዚህ ፊቴን ከእነርሱ ሰወርሁ፤ ለጠላቶቻቸው አሳልፌ ሰጠኋቸው፤ ሁሉም በሰይፍ ወደቁ:: [24]እንደ ርኵሰታቸውና እንደ በደላቸው መጠን ፈረድሁባቸው፤ ፊቴንም ከእነርሱ ሰወርሁ::

[25]“ስለዚህ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ ያዕቆብን አሁን ከስደት እመልሰዋለሁ፤[n] ለእስራኤል ሕዝብ ሁሉ እራራለሁ፤ ስለ ቅዱስ ስሜም እቀናለሁ:: [26]የሚያስፈራቸው ማንም ሳይኖር በምድራቸው በሰላም በሚኖሩበት ጊዜ፣ ውርደታቸውንና ለእኔ ታማኝ ሆነው ያልኖሩበትን ዘመን ይረሳሉ:: [27]ከአሕዛብ ምድር መልሼ ሳመጣቸው፣ ከጠላቶቻቸው አገር ስሰበስባቸው የራሴን ቅድስና በእነርሱ በኩል በብዙ ሕዝቦች ፊት አሳያለሁ:: [28]በአሕዛብ መካከል እንዲሰደዱ ባደርግም፣ አንድም ሳላስቀር ወደ ገዛ ምድራቸው እመልሳቸዋለሁ፤ ከዚያም እኔ እግዚአብሔር አምላካቸው እንደ ሆንሁ ያውቃሉ:: [29]ከእንግዲህ ፊቴን ከእነርሱ አልሰውርም፤ መንፈሴን በእስራኤል ቤት ላይ አፈሳለሁና፤ ይላል ጌታ እግዚአብሔር::”

## አዲሱ ቤተ መቅደስ

**40** በተሰደድን በሃያ አምስተኛው ዓመት፣ በዓመቱ መጀመሪያ፣ በዐሥረኛው ቀን፣ ከተማዪቱ በወደቀች በዐሥራ አራተኛው ዓመት፣ በዚያው ዕለት የእግዚአብሔር እጅ በላዬ ነበር፤ እርሱም ወደዚያ ወሰደኝ:: [2]በእግዚአብሔር ራእይ ወደ እስራኤል ምድር አመጣኝ፤ ከፍ ባለ ተራራ ላይ አኖረኝ፤ ከተራራውም በስተ ደቡብ፣ ከተማ የሚመ

[n]25 ወይም አሁን የያዕቆብን ዕድል ዐድሳለሁ

39+17 ኢዮ15+23፤ ሕዝ32+4
39+18 መዝ22+12፤ ኤር51+40
39+19 ዘሌ3+9
39+20 ኢሳ59+9፤ ኤር12+9፤ ራእ 19+17-18
39+21 ዘፀ9+16፤ ኢሳ37+20፤ ሕዝ 38+16
39+23 ኢሳ1+15፤ 59+2፤ ኤር22+8-9፤ 44+23
39+24 2ነገ17+23፤ ኤር2+17:19፤4+18፤ ሕዝ7+22፤ዳን9+7
39+25 ኢሳ27+12-13፤ ኤር30+18፤ 33+7፤ ሕዝ16+53
39+26 1ነገ4+25፤ ኢሳ17+2፤ ኤር32+37፤ ሕዝ34+28፤38+8፤ ሚክ4+4
39+27 ሕዝ37+21
39+28 መዝ147+2፤ ሕዝ36+23:36
39+29 ዘዳ31+17፤ ኢሳ11+2፤ ሕዝ16+42፤37+9፤ ሐሥ2+17
40+1 2ነገ25+7፤ ኤር39+1-10፤52+4-11፤ ሕዝ1+3፤29+17
40+2 ዘፀ24+10፤ ኤር31+12፤ ሕዝ17+22፤ ዳን7+1:7፤ ራእ21+10

39+17 *ማንኛውንም ዐይነት ወፍ ... ጥራ ... መሥዋዕት፤* ለዚህ የተለያዩ ትርጓሜዎች ተሰጥተዋል፤ እነርሱም፦ 1/ ጠላቶች በሙሉ የሞቱና የተቀበሩ እስከሆኑ ድረስ፣ ከቍ 17-20 ያለው ክፍል ምስል አዘል ግጥም ሊሆን ይችላል:: 2/ ይሁን እንጂ፣ ይህ ምንባብ ከቍ 4 አኳያ ቃል በቃል ሲተረጐም ሙታኑ በሙሉ በአንድ ጊዜ አልተቀበሩም ማለት ነው:: 3/ ከቍ 17-20 የተገለጸው፣ ከቍ 9-16 ያለውን ሐሳብ በሌላ መልክ አቅርቦታል (ኢሳ 34+6፤ ኤር46+10፤ ሶፎ1+7 ይመ):: እነዚህን መሥዋዕት አድርጎ በተለዋጭ ዘይቤ ማቅረቡ፣ በኢያሪኮ እንደ ሆነው ሁሉ (ኢሱ6+17 ይመ፤ አማራጭ ትርጕሙን ይመ) እንዲሁም እርም አድርጎ ለእግዚአብሔር ፍርድ አሳልፎ መስጠትን ያመለክታል::

39+18 *የኀያላን ሰዎችን ሥጋ ትበላላችሁ፤* ነጣቂ አሞሮች እንደሚያደርጉት ማቍሰልንና ማድማትን የሚያመለክት ነው (ራእ19+17-21 ይመ):: *እንደ፤* የሰዎቹ አስከሬን ለመሥዋዕት ከሚቀርቡ እንስሳት ጋር ተነጻጽሮአል:: *ባሳን፤* ከገሊላ ባሕር በስተ ምሥራቅ የሚገኝ የበለጸገ የግጦሽ መሬት ሲሆን፣ በሰቡ ከብቶችና (ዘዳ32+14፤ መዝ22+12፤ አሞ4+1) በዝግባ ዛፎች የታወቀ (27+6፤ ኢሳ2+13) ምድር ነው::

39+19 *ስብ ትበላላችሁ ... ደም ትጠጣላችሁ፤* የእግዚአብሔርን በዓል በተጨማሪ የሚያመለክትና ስብና ደምም ለእግዚአብሔር ብቻ የሚቀርቡ የመሥዋዕት ዐይነቶች መሆናቸውን የሚገልጽ ነው (44+15፤ ዘሌ3+17)::

39+20 *በገበታዬም፤* መሥዋዕቱ የሚቀርብበትን መሠዊያ የሚያመለክት ነው:: በአዲሱ ቤተ መቅደስ ስላሉት ገበታዎች የተሰጠውን ገለጻ በ40+38-43 እና 41+22 ይመ::

39+21 *ክብሬን፤* እግዚአብሔር በዚች ዓለም ተገኝቶ በገሀድ መታየቱን የሚያመለክት ነው (የ1+28 ማብ ይመ)::

39+22-23 *የእስራኤል ቤት ... ያውቃሉ:: አሕዛብም ... ያውቃሉ፤* እስራኤላውያንን በማዳኑ፣ እነርሱና አሕዛብ እርሱን እንዲያውቁት ሁሉ፣ (ዘፀ6+7፤ 7+5:17፤ 10+2፤ 14+18፤ 16+6-7:12፤ ኢሱ3+10፤ 4+24 ይመ፤ ⁄ ከኢሱ2+9-11፤ 5+1 ጋር ያነጻጽሩ)፣ አሁን ደግሞ እስራኤላውያንን በኀጢአታቸው ምክንያት ሲቀጣቸው፣ እነርሱም አሕዛብም ያውቁታል (ቍ 27)::

39+23 *ፊቴን ከእነርሱ ሰወርሁ፤* እግዚአብሔር በሕዝቡ ያለመደሰቱን የሚገልጽ ነው (መዝ30+7፤ ኢሳ54+8፤ 57+17 ይመ)::

39+24 *እንደ ርኵሰታቸውና እንደ በደላቸው፤* ጕልህ ሆኖ በም22 ላይ ተገልጾአል፤ እንዲሁም ከም6-24 ላይም ተጠቅሶ ይገኛል::

39+25 *ያዕቆብ፤* በ20+5 ላይ እንደተገለጸው፣ የእስራኤልን ሕዝብ ማለት ነው:: በዚህ ቍጥር ውስጥ ያለው ተጓዳኝ ሐሳብ ይህንኑ የሚደግፍ ነው:: *ስለ ቅዱስ ስሜም፤* የ20+9 ማብ ይመ::

39+26 *ውርደታቸውን ... ይረሳሉ፤* ቀደም ባለው ጊዜ የነበረውን የውርደት ትዝታ (6+9፤ 20+43፤ 36+31) እዚህ ላይ ፈጽሞ ተደምስሶአል::

39+27 *የራሴን ቅድስና በእነርሱ በኩል ... አሳያለሁ፤* ከከፉ መንገዱ በተመለሰ ሕዝብ መካከል፣ እግዚአብሔር ራሱን በአዲስ መልክ ይገልጣል (ከ20+41፣ 28+25፤ 36+23 ጋር ያነጻጽሩ)::

39+28 *ያውቃሉ፤* የቍ 22 ማብ ይመ::

39+29 *መንፈሴን ... አፈሳለሁና፤* ኀይል የሚሰጠውን የእግዚአብሔርን መንፈስ መስጠት ማለት ነው (11+19፤ 36+26-27፤ 37+14 ይመ)::

40+1 *በተሰደድን፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተጠቀሱት ቀናት በሙሉ መሠረት ያደረጉት በ597 ዓ.ቅ.ክ. የነበረውን ምርኮ ነው፤ (በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የተገለጸውን የቀናት መግለጫ በገጽ 1222 ላይ ይመ)፤ ነገር ግን እዚህ ላይና በ33+21 ላይ ምርኮው ለየት ባለ መንገድ ተገልጾአል (1+2 ይመ):: *ሃያ አምስተኛው ዓመት .መጀመሪያ፣ ... በዐሥረኛው፤* ሚያዝያ 28 ቀን 573 ዓ.ቅ.ክ. ነው:: *በዓመቱ መጀመሪያ፤* በዕብራይስጥ ሮሽ ሃሻናህ የሚባለውና የታወቀው የአይሁድ የዘመን መለወጫ በዓል ነው:: የሚውለውም በመስከረም ወይም በጥቅምት ወር ነው:: ይሁን እንጂ፣ በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ ያለው ለየት ያለና ከዚያ በፊት የነበረውን የዘመን መቍጠሪያ ማለት ነው፤ ስለዚህም ከላይ የተጠቀሰው የበልግ ወቅት ይህንኑ የዘመን አቈጣጠር ነው (የዘሌ 23+24 ማብ ይመ):: *የእግዚአብሔር እጅ በላዬ ነበር፤* የ1+3 ማብ ይመ::

40+2 *በእግዚአብሔር ራእይ፤* ሦስቱንም የሕዝቅኤል ዐበይት ራእዮች ያስታውሰናል (1+1፤ 8+3 ይመ):: *ከፍ ባለ ተራራ፤* የጽዮን ተራራ ነው፤ ይህ ተራራ በሌሎቹ ትንቢታዊ ራእዮች

ስሉ ሕንጻዎች ነበሩ:: [3]ወደዚያ ወሰደኝ፤ እነሆ መልኩ ናስ የሚመስል ሰው አየሁ፤ እርሱም የሐር ገመድና መለኪያ ዘንግ በእጁ ይዞ በመግቢያው በር ላይ ቆሞ ነበር:: [4]ሰውየውም እንዲህ አለኝ፤ "የሰው ልጅ ሆይ፤ በዐይንህ እይ፤ በጆሮህ ስማ፤ የማሳይህንም ሁሉ ልብ ብለህ አስተውል፤ ወደዚህ የመጣኸው ለዚህ ነውና ያየኸውንም ሁሉ ለእስራኤል ቤት ንገር::"

## ወደ ውጩ አደባባይ የሚያወጣው የምሥራቅ በር

[5]የቤተ መቅደሱን ዙሪያ ሙሉ በሙሉ የከበበ ቅጥር አየሁ፤ በሰውየውም እጅ ርዝመቱ ስድስት ክንድ የሆነ መለኪያ ዘንግ አየሁ፤ እያንዳንዱ ክንድ፣ አንድ ክንድ ከስንዝር ነበር፤ እርሱም ቅጥሩን ለካው፤ ስፋቱ አንድ መለኪያ ዘንግ ሲሆን፣ ቁመቱም እንዲሁ አንድ መለኪያ ዘንግ ነበር::

[6]ከዚያም በምሥራቅ ትይዩ ወዳለው በር መጣ፤ ደረጃዎቹን ወጥቶ የበሩን መግቢያ መድረክ ለካ፤ ቍመቱም አንድ ዘንግ ነበር::[a] [7]የዘብ ጠባቂ ቤቶች፣ ቁመታቸው አንድ መለኪያ ዘንግ፣ ወርዳቸውም አንድ መለኪያ ዘንግ ነበር፤ በቤቶቹም መካከል ያሉት ግንቦች ውፍረት አምስት ክንድ ነበር:: ከቤተ መቅደሱ ፊት ለፊት ባለው መተላለፊያ በረንዳ አጠገብ በውስጥ በኩል ያለው የበሩ መድረክ ወለል አንድ ዘንግ ነበር::

[8]ከዚያም የመግቢያውን በር መተላለፊያውን በረንዳ ለካ፤ [9]ቍመቱ[b] ስምንት ክንድ፣ የዐምዶቹም ውፍረት ሁለት ክንድ ነበር:: የመግቢያው በር መተላለፊያ በረንዳ፣ ከቤተ መቅደሱ ትይዩ ነው::

[10]በምሥራቁ በር ግራና ቀኝ መጠናቸው እኩል የሆነ ሦስት ሦስት የዘብ ቤቶች ነበሩ፤ በመካከላቸው ወጣ ወጣ ብለው የሚታዩትም ግንቦች ተመሳሳይና እኩል ነበሩ:: [11]ከዚያም የበሩን ስፋት ለካ፤ ወርዱ ዐሥር ክንድ፣ ርዝመቱም ዐሥራ ሦስት ክንድ ነበር:: [12]በእያንዳንዱ ዘብ ቤት ፊት ለፊት ከፍታው አንድ ክንድ የሆነ መከለያ የግንብ ዐጥር አለ፤ የዘብ ቤቶቹም ስፋት እኩል በኩል ስድስት ክንድ ነበር:: [13]ከዚያም ከዘብ ቤቱ የኋላ ግድግዳ ጀምሮ እስከ ሌላው ጫፍ ድረስ ያለውን የመግቢያ በር ለካ፤ ከአንዱ መከለያ ግድግዳ እስከ ሌላው መከለያ ግድግዳ ያለው ርቀት ሃያ አምስት ክንድ ነበር:: [14]በመግቢያው በር ዙሪያ ባሉት ወጣ ወጣ ባሉት ግንቦች ሁሉ ፊት ለፊት ያለውን ቦታ ለካ፤ ሥልሳ ክንድም ነበር:: የተለካውም ከአደባባዩ[c] ፊት ለፊት እስካለው መተላለፊያ በረንዳ[d] ድረስ ነበር:: [15]ከበሩ መግቢያ እስከ መተላለፊያ በረንዳው መጨረሻ ድረስ ያለው ርቀት አምሳ ክንድ ነበር:: [16]ክፍሎቹ እንደ መተላለፊያ በረንዳዎቹ ከግራና ከቀኝ በኩል ትንንሽ መስኮቶች አሏቸው:: በዙሪያው ያሉ መስኮቶች በመግቢያው በር ፊት ለፊት የነበሩ ሲሆን፣ በእያንዳንዱ ክፍል ግራና ቀኝ ግድግዳ ላይ ደግሞ የዘንባባ ዛፍ ተቀርጾበታል::

## የውጩ አደባባይ

[17]ከዚያም ወደ ውጩ አደባባይ አመጣኝ፤ እዚያም በአደባባዩ ዙሪያ የተሠሩ ክፍሎችና ድንጋይ የተነጠፈበት መመላለሻ አየሁ፤ በመመላለሻውም ዙሪያ ሠላሳ ክፍሎች ነበሩ:: [18]የታችኛው ንጣፍ ወለል ከመግቢያው በር ጋር ተያይዞ የተሠራ ሲሆን፣

40+3 ሕዝ1+7፤ 47+3፤ዘካ2+1-2፤ራእ 1+15፤11+1፤21+15
40+4 ዘዳ6+6፤ኤር 26+2፤ሕዝ44+5
40+5 ሕዝ42+20
40+6 ሕዝ8+16
40+7 ቍ36
40+14 ዘፀ27+9
40+16 ቍ21-22፤ 2ዜና3+5፤ሕዝ41+26
40+17 ራእ11+2፤ ሕዝ41+6፤42+1

[a]6 ከሰብዓ ሊቃናት ጋር ተመሳሳይ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *የመጀመሪያው ጕበን ርዝመቱ አንድ ዘንግ ነበር* ይላል
[b]8-9 በብዙ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች በሰብዓ ሊቃናት፣ በቩልጌትና በሱርስቱም እንዲሁ ሲሆን አብዛኛዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ግን *በቤተ መቅደሱ ትይዩ ያለ የመግቢያ በር ነው፤ አንድ ክንድ ነበር 9. ከዚያም የመግቢያ በሩን መተላለፊያ በረንዳ፣ ለካው፤ ...* ይላሉ
[c]14 ሰበዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ወጣ ያለ ግንብ* ይለዋል
[d]14 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም አይታወቅም

ውስጥም እጅግ ከፍ ያለ ትልቅ ተራራ ሆኖ ቀርቦአል (17+22፤ ኢሳ2+2፤ ሚክ4+1፤ ዘካ14+10):: "ከፍ" የሚለው ቃል፣ እዚህ ላይ የሚያመለክተው ለእግዚአብሔር መንግሥት መቀመጫነት ተገቢ ቦታ መሆኑን ነው:: *በስተ ደቡብ፤* ከተማዪቱ በስተ ደቡብ ባለው የተራራ ተዳፋት ላይ የምትገኝ ስለሆነች፣ ተራራው የሚገኘው በስተ ሰሜን በኩል ነው (ከመዝ48 ጋር ያነጻጽሩ፤ መዝ48+2 እና ማብ ይመ)::

40+3 *ናስ የሚመስል፤* ሰብአዊ ፍጡር አለመሆኑን ያመለክታል:: *የሐር ገመድ፤* በ47+3 ላይ እንደ ተጠቀሰው ረጅም ርቀት የሚለካበት ነው:: *መለኪያ ዘንግ፤* እስከ ሦስት ሜትር ያህል ለሚሆኑ አጫጭር ርዝመቶች መለኪያ ነው:: *በመግቢያው በር ላይ፤* ምናልባት የውጪውን አደባባይ ሳይሆን አይቀርም (ቍ17-19 ይመ)::

40+5 የቤተ *መቅደሱን ዙሪያ ሙሉ በሙሉ የከበበ ቅጥር፤* መንፈሳዊውን ስፍራ ከሌላው የሚከልል ማለት ነው:: *ርዝመቱ ስድስት ክንድ፤* አጭር የሆነውን የክንድ መለኪያ ሳይሆን፣ ከዚህ በፊት የነበረውን ረጅሙንና አሮጌውን የክንድ መለኪያ (53 ሴንቲ ሜትር) በመጠቀም ሕዝቅኤል ለአዲሱ ኅብረተ ሰብ የቀድሞውን መለኪያ በመጠቀም ነገራቸው (2ዜና 3+3 ይመ)::

40+6 *በምሥራቅ ትይዩ ወዳለው በር፤* የውጭው አደባባይ በር ነው:: በውጭው አደባባይ ላይ ያሉት ሦስቱ በሮች (የምሥራቁ፣ የሰሜኑና የደቡብ)፣ በውስጠኛው አደባባይ ካሉት ሦስት በሮች ጋር ተመሳሳይ ናቸው (ቍ32)፤ በየጐኑ ሦስት ሦስት የሆኑ በድምሩ ስድስት የዘብ ቤቶችና መተላለፊያ በረንዳዎች አሉት (ቍ8-9):: እንዲሁም ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆኑ የበር ፕላን በመጊዶ፣ በጌዝርና በሐይር ተገኝተዋል፤ እነዚህም በሰሎሞን ዘመነ መንግሥት የተሠሩ ነበሩ (1ነገ9+15 ይመ):: ዘበኞቹ የቤተ መቅደሱን አካባቢ ሊያረክስ የሚችለውን ማንኛውንም ሰው አያስገቡም (ዕዝ2+62 ይመ):: *ደረጃዎቹን ወጥቶ፤* ወደ ቤተ መቅደሱ ከሚወስዱት ሦስት ቦታ ካሉት ደረጃዎች፣ ይህ የመጀመሪያው ነው:: ይኸውም ሰባት ደረጃዎች አሉት (ቍ22)፤ የሚቀጥለው ማለትም በውስጠኛው አደባባይ ያለው ስምንት ደረጃዎች ሲኖሩት (ቍ31)፣ የመጨረሻው (ቤተ መቅደሱ ውስጥ ያለው) ዐሥር ደረጃዎች አሉት (ቍ49፤ አማራጭ ትርጕሙን ይመ):: ምናልባት የደረጃዎቹ ቍጥር እየጨመረ መሄድ፣ "የቅድስናን" ወይም የመንፈሳዊነትን ደረጃ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል::

40+9 *የመግቢያው በር መተላለፊያ በረንዳ፣ ከቤተ መቅደሱ ትይዩ ነው፤* ይህ መተላለፊያ በረንዳ የሚገኘው ለቤተ መቅደሱ ትይዩ ሆኖ ነው (ቍ34 ይመ)::

40+10 *ሦስት የዘብ ቤቶች፤* እነዚህ የዘብ ቤቶች በቍ7 ላይ ተጠቅሰዋል::

40+16 *የዘንባባ ዛፍ፤* በሰሎሞን ቤተ መቅደስ ውስጥ ያለውን ዐይነት ማለት ነው (1 ነገ6+29:32:35 ይመ)::

40+17 *ሠላሳ ክፍሎች፤* የእነዚህ ክፍሎች ትክክለኛ ቦታ የት እንደ ሆነ አልተገለጸም፤ ምናልባት ሕዝቡ እንዲጠቀምበት የተሠሩ ሊሆን ይችላል (ኤር35+2:4 ይመ)::

# የሕዝቅኤል ቤተ መቅደስ

ሀ. ቅጥር (40:5፣ 16-20)
ለ. የምሥራቅ በር (40:6-14፣16)
ሐ. ደጀ ሰላም (40:8)
መ. የውጭ አደባባይ (40:17)
ሠ. ወለል (40:17)
ረ. የውስጠኛ አደባባይ (40:19)
ሰ. የሰሜን በር (40:20-22)
ሸ. የውስጠኛ አደባባይ (40:23)
ቀ. የደቡብ በር (40:24-26)
በ. የደቡብ ውስጠኛ አደባባይ (40:27)
ተ. መግቢያ (40:28-31)
ቸ. መግቢያ (40:32-34)
ኀ. መግቢያ (40:35-38)
ነ. የካህናት ክፍሎች (40:44-45)
ኘ. አደባባይ (40:47)
አ. የመቅደሱ ደጀ ሰላም (40:48-49)
ከ. የመቅደሱ ውጪ (41:1-2)
ኸ. ቅድስተ ቅዱሳን (41:3-4)
ወ. የመቅደሱ ግንብ (41:5-7፣9፣11)
ዐ. መሠረት (41:8)
ዘ. ክፍት ቦታ (41:10)
ዠ. በምዕራብ ያለ ግንብ (41:12)
የ. የካህናት ክፍሎች (42:1-12)
ደ. መሠዊያ (43:13-17)
ጀ. የማዘጋጃ ክፍሎች (40:39-43)
ገ. ማብሰያ ክፍል (46:19-20)
ጠ. ማዕድ ቤቶች (46:21-24)

ሕዝቅኤል የተጠቀመው መለኪያ በአይሁድ ዘንድ ከተለመደው («አንድ ክንድ ከጋት» ሕዝ 40:5) ከፍ የሚል 51.81 ሳ.ሜ. ነው።

ይህ ቤተ መቅደስ በሕዝቅኤል ራእይ ብቻ የተገለጠ (40:2) እንጂ እንደ ሰለሞን፣ ዘሩባቤልና ሄሮድስ ቤተ መቅደስ የተሠራ አይደለም።



ስፋቱ እንደ በሮቹ ርዝመት መጠን ነበር:: [19]ከዚያም ከታችኛው መግቢያ በር ፊት ጀምሮ እስከ ውስጠኛው አደባባይ ፊት ድረስ ያለውን ርቀት ለካ፤ በምሥራቅም ሆነ በሰሜን በኩል ያለው ርቀት አንድ መቶ ክንድ ነበር::

## የሰሜኑ በር

[20]ከዚያም በሰሜን ትይዩ ያለውን፣ ወደ ውጩ አደባባይ የሚያመራውን በር ርዝመትና ወርድ ለካ:: [21]እንደ መጀመሪያው በር ሁሉ ይኸኛውም በየጐኑ ያሉት ሦስት ሦስት የዘብ ቤቶች፣ በየመካከሉ ወጣ ወጣ ያሉ ግንቦችና መተላለፊያ በረንዳዎቹ መጠናቸው እኩል ነበር:: ርዝመቱ አምሳ ክንድ፣ ወርዱም ሃያ አምስት ክንድ ነበር:: [22]መስኮቶቹ፣ መተላለፊያ በረንዳዎቹና የዘንባባ ዛፍ ቅርጾቹ ልካቸው በምሥራቁ በር ካሉት ጋር ተመሳሳይ ነበር:: ወደዚያ የሚያመሩ ሰባት ደረጃዎች አሉ፤ መተላለፊያ በረንዳዎቹም ከእነርሱ ጋር ትይዩ ነበር:: [23]ልክ በምሥራቅ በኩል እንዳለው ሁሉ፣ ከሰሜኑ በር ጋር ትይዩ የሆነ ወደ ውስጠኛው አደባባይ የሚያመራ በር አለ:: ከአንዱ በር እስከ ሌላኛው በር ያለውን ለካው፤ ይህም አንድ መቶ ክንድ ነበር::

## የደቡቡ በር

[24]ከዚያም ወደ ደቡብ አቅጣጫ መራኝ፤ እዚያም ፊቱን ወደ ደቡብ ያደረገ በር አየሁ፤ እርሱም የውስጠኛውን ግድግዳና መተላለፊያ በረንዳውን ለካ፤ የእነዚህም መጠን እንደ ሌሎቹ በሮች ነበር:: [25]የመግቢያው በርና መተላለፊያ በረንዳው እንደ ሌሎቹ ሁሉ በዙሪያው ጠባብ መስኮቶች ነበሩት፤ ርዝመቱ አምሳ ክንድ፤ ወርዱም ሃያ አምስት ክንድ ነበር:: [26]ከመተላለፊያ በረንዳው ትይዩ የሆኑ ሰባት ደረጃዎች ወደ መግቢያው በር ያመራሉ፤ ወጣ ወጣ ብለው በሚታዩ ግድግዳዎችም ላይ የዘንባባ ቅርጽ አለ:: [27]ውስጠኛው አደባባይ ደግሞ ከደቡብ ጋር ትይዩ የሆነ በር አለው፤ እርሱም ከዚህ በር አንሥቶ በደቡብ አቅጣጫ እስካለው እስከ ውጭው በር ድረስ ለካው፤ ይህም አንድ መቶ ክንድ ሆነ::

## ወደ ውስጠኛው አደባባይ የሚያስገቡ በሮች

[28]ከዚያም በደቡብ በር በኩል ወደ ውስጠኛው አደባባይ አመጣኝ፤ የደቡብንም በር ለካው፤ መጠኑም እንደ ሌሎቹ በሮች ነበር:: [29]የዘብ ቤቶቹ፣ በየመካከሉ ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦችና መተላለፊያ በረንዳዎቹ መጠናቸው ከሌሎቹ ጋር ተመሳሳይ ነበር:: መግቢያው በርና መተላለፊያ በረንዳዎቹ በዙሪያቸው መስኮቶች ነበሯቸው:: ርዝመቱ አምሳ ክንድ ወርዱም ሃያ አምስት ክንድ ነበር:: [30]በውስጠኛው አደባባይ ዙሪያ ያሉት የመግቢያው በር መተላለፊያ በረንዳዎቹ ርዝመት ሃያ አምስት ክንድ ሲሆን፣ ወርዳቸው ደግሞ አምስት ክንድ ነበር:: [31]መተላለፊያ በረንዳው ከውጭው አደባባይ ጋር ትይዩ ነው፤ የዘምባባ ዛፎች በዐምዶቹ ላይ ተቀርጸዋል፤ እስከ መግቢያው ድረስም ስምንት ደረጃዎች ነበሩት::

[32]ከዚያም በምሥራቅ በኩል ወደ ውስጠኛው አደባባይ አመጣኝ፤ መግቢያ በሩንም ለካው፤ መጠኑም ከሌሎቹ ጋር ተመሳሳይ ነበር:: [33]የዘብ ቤቶቹ፣ ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦችና መተላለፊያ በረንዳዎቹ መጠናቸው ከሌሎቹ ጋር ተመሳሳይ ነበር፤ መግቢያው በርና መተላለፊያ በረንዳው ዙሪያውን መስኮቶች ነበሩት፤ የዚህም ርዝመቱ አምሳ ክንድ፣ ወርዱ ሃያ አምስት ክንድ ነበር:: [34]መተላለፊያ በረንዳው ከውጩ አደባባይ ትይዩ ነው፤ በዐምዶቹ ላይ የዘንባባ ዛፍ ተቀርጾአል፤ እስከ መግቢያ ድረስም ስምንት ደረጃዎች ነበሩት::

[35]ከዚያም ወደ ሰሜን በር አመጣኝ፤ ለካውም፤ መጠኑም ከሌሎቹ ጋር ተመሳሳይ ነበር:: [36]የዘብ ቤቶቹ፣ ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦቹና መተላለፊያ በረንዳው መጠናቸው ከሌሎቹ ጋር ተመሳሳይ ነበር፤ በዙሪያውም መስኮቶች ነበሩት:: የዚህም ርዝመቱ አምሳ ክንድ ወርዱም ሃያ አምስት ክንድ ነበር:: [37]መተላለፊያ በረንዳው[f] ከውጩ አደባባይ ትይዩ ነው፤ በዐምዶቹም ላይ የዘንባባ ዛፍ ተቀርጾአል፤ እስከ መግቢያው ድረስም ስምንት ደረጃዎች ነበሩት::

## መሥዋዕት የሚዘጋጅባቸው ክፍሎች

[38]በእያንዳንዱ የውስጥ መግቢያ በር መተላለፊያ በረንዳ አጠገብ፣ የሚቃጠል መሥዋዕት የሚታጠብበት በር ያለው ክፍል አለ:: [39]በመግቢያው በር ላይ ባለው መተላለፊያ በረንዳው ሥር በግራና በቀኝ የሚቃጠል መሥዋዕት፣ የኀጢአትና የበደል መሥዋዕት የሚታረዱበት ሁለት ሁለት ጠረ

40+19 ቍ23:27፤ ሕዝ46+1
40+21 ቍ7:30
40+22 ቍ16:26:49
40+23 ቍ19
40+24 ቍ32:35
40+25 ቍ33
40+26 ቍ22
40+27 ቍ19:32
40+28 ቍ35
40+29 ቍ7:25
40+30 ቍ21
40+31 ቍ22:34:37
40+32 ቍ24
40+33 ቍ7
40+34 ቍ22
40+35 ቍ24፤ ሕዝ 44+4፤47+2
40+36 ቍ7
40+37 ቍ22:34
40+38 2ዜና4+6፤ ሕዝ42+13
40+39 ቍ42፤ ዘሌ 4+3:28፤7+1፤ ሕዝ 46+2

[f]37 ሰብዓ ሊቃናቱም (በተጨማሪ ቍ31 እና 34 ይመ) እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *መቃኖች* ይላል

40+19 *አንድ መቶ ክንድ፤* ከውጭው ግድግዳ እስከ ውስጠኛው ግድግዳ ያለው ርቀት አምሳ ሁለት ሜትር ያህል ሲሆን፣ ይኸውም የውጭው አደባባይ ስፋት ነው::

40+20 *በሰሜን ትይዩ ያለውን ... በር፤* ይኸኛው በር፣ ከደቡብና (ቍ 24) ከምሥራቁ በር ጋር ተመሳሳይ ነው::

40+22 *ሰባት ደረጃዎች፤* የቍ6 ማብ ይመ::

40+28 *በደቡብ በር፣* ይህ በር በግልጽ ባይጠቀስም የውስጠኛው ግንብ እንደ ሆነ ይገመታል:: *መጠኑ እንደ ሌሎቹ በሮች ነበር፤* በውጭ እንዳሉት ግንቦች ማለት ነው (የቍ6 ማብ ይመ)::

40+34 *ስምንት ደረጃዎች፤* የቍ6 ማብ ይመ::

40+38 *በእያንዳንዱ የውስጥ መግቢያ በር መተላለፊያ በረንዳው፤* እነዚህ መተላለፊያ በረንዶች ከቤተ መቅደሱ ራቅ ያሉ ሲሆኑ፣ በውስጠኛው አደባባይ አጠገብ ወደ ውስጥ መግቢያ በር ላይ የሚገኙ ናቸው:: *የሚታጠብበት፤* የውስጥ ብልቶችና እግሮች ይታጠቡ ነበር (ዘሌ1+9)::

40+39 *የሚቃጠል መሥዋዕት፤* ምናልባት ይህ ከቈዩት የመሥዋዕት ዐይነቶች አንዱ ሊሆን ይችላል:: እንስሳው ሙሉ በሙሉ ለእግዚአብሔር የተቀደሰ ሆኖ ይቃጠላል (ዘሌ1 ይመ):: *የኀጢአትና የበደል መሥዋዕት፤* በዘሌ4-7 ባለው ክፍል ተብራርቶ ይገኛል:: በከፍተኛ ደረጃ የሚከበሩት የኅብረት መሥዋዕቶች፣

ጴዛዎች አሉ:: [40]ከመግቢያው በር ላይ ባለው መተላለፊያ በረንዳ በስተ ውጭው ግንብ ወደ ሰሜን በር መግቢያ ላይ ባሉት ደረጃዎች አጠገብ ከግራና ከቀኝ ሁለት ሁለት ጠረጴዛዎች ይገኛሉ:: [41]ስለዚህ በአንዱ በር በኩል አራት፣ በሌላውም በኩል አራት ጠረጴዛዎች፤ መሥዋዕቱ የሚታረድባቸው በድምሩ ስምንት ጠረጴዛዎች አሉ ማለት ነው:: [42]ለሚቃጠለው መሥዋዕት መገልገያ የሆኑ፣ ከተጠረበ ድንጋይ የተሠሩ አራት ጠረጴዞች ነበሩ፤ የእያንዳንዳቸው ርዝመት፣ ወርድና ቁመት አንድ ክንድ ተኩል ነበር፤ በእነዚህም ላይ ለሚቃጠለው መሥዋዕትና ለሌላውም መሥዋዕት ማረጃ የሚሆኑ መሣሪያዎች ይቀመጡባቸው ነበር:: [43]እንዲሁም አንዳንድ ስንዝር የሚሆኑ ሁለት ባት ያላቸው ሜንጦዎች በግንቡ ዙሪያ ተንጠልጥለው ነበር፤ ጠረጴዛዎቹም የመሥዋዕቱ ሥጋ ማስቀመጫ ነበሩ::

### ለካህናት የተመደቡ ክፍሎች

[44]በውስጠኛው አደባባይ፣ ከውስጠኛው በር ውጭ፣ ሁለት ክፍሎች ነበሩ፤ አንዱ[ሀ] በደቡብ[ለ] ትይዩ በሰሜን በር በኩል ሲሆን፣ ሌላው በሰሜን ትይዩ በደቡብ በር በኩል ነበር:: [45]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "በደቡብ ትይዩ ያለው ክፍል በቤተ መቅደስ ውስጥ ለሚያገለግሉ ካህናት ሲሆን፣ [46]በሰሜን ትይዩ ያለው ክፍል ደግሞ በመሠዊያው ላይ ለሚያገለግሉ ካህናት ነው:: እነዚህም የሳዶቅ ልጆች ሲሆኑ፣ *በእግዚአብሔር ፊት* ቀርበው ማገልገል የሚችሉ ሌዋውያን እነርሱ ብቻ ናቸው::"

[47]ከዚያም አደባባዩን ለካው፤ ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ፣ ወርዱ መቶ ክንድ እኩል በእኩል ባለ አራት ማእዘን ነበር:: መሠዊያውም በቤተ መቅደሱ ፊት ለፊት ነበር::

### ቤተ መቅደሱ

[48]ወደ ቤተ መቅደሱም መተላለፊያ በረንዳ አመጣኝ፤ የመተላለፊያ በረንዳዎቹን ዐምዶች ለካ፤ በአንዱ በኩል አምስት ክንድ በሌላውም እንዲሁ አምስት ክንድ ነበር:: የመግቢያው በር ርዝመት ዐሥራ አራት ክንድ ሲሆን፣ ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦች ስፋት በአንዱ በኩል ሦስት ክንድ፣ በሌላውም እንዲሁ ሦስት ክንድ ነበሩ::[ሐ] [49]የመተላለፊያው በረንዳ ርዝመት ሃያ ክንድ፣ ከፊት እስከ ኋላ ያለውም ወርድ ዐሥራ ሁለት[መ] ክንድ ነበር:: ወደ ቤተ መቅደሱም የሚያደርሱ ዐሥር ደረጃዎች የነበሩ ሲሆን፣ በየዐምዱም ጐንና ጐን ምሰሶዎች ነበሩ::

40+42 ቍ39፤ ዘፀ20+25
40+45 1ዜና9+23
40+46 ዘኍ16+5፤ 18+5፤2ሳሙ8+17፤ ዕዝ7+2፤ሕዝ42+13፤ 43+19፤44+15፤45+4፤48+11
40+47 ሕዝ41+13-14
40+48 1ነገ6+2
40+49 ቍ22፤1ነገ6+3፤7+15

## 41

[1]ከዚያም ወደ መቅደሱ አገባኝ፤ ዐምዶቹንም ለካ፤ የዐምዶቹም ወርድ[ሠ] በአንዱ በኩል ስድስት ክንድ፣ በሌላውም በኩል ስድስት ክንድ ነበር:: [2]የመግቢያውም በር ወርድ ዐሥር ክንድ ሲሆን፣ በግራና በቀኝ በኩል ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦች ወርድ አምስት ክንድ ነበር:: ደግሞም የውስጡን መቅደስ ለካ፤ ርዝመቱ አርባ ክንድ፣ ወርዱም ሃያ ክንድ ነበር::

[3]ከዚያም ወደ ውስጥ ገባ፤ የመግቢያውን ዐምዶች ለካ፤ የእያንዳንዱም ወርድ ሁለት ክንድ ነበር:: የመግቢያውም ወርድ ስድስት ክንድ ሲሆን፣ ግራና ቀኝ ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦች ወርድ ደግሞ ሰባት ክንድ ነበር:: [4]እርሱም የውስጠኛውን መቅደስ ርዝመት ለካ፤ ሃያ ክንድ ነበር፤ ወርዱም የውጪውን ግድግዳ ጨምሮ ሃያ ክንድ ነበር፤ እርሱም፣ "ይህ ቅድስተ ቅዱሳን ነው" አለኝ::

[5]ከዚያም የቤተ መቅደሱን ግንብ ለካ፤ ውፍረቱ ስድስት ክንድ ነው፤ በቤተ መቅደሱ ግንብ ዙሪያ ግራና ቀኝ ያለው የእያንዳንዱ ክፍል ወርድ አራት ክንድ ነበር:: [6]ግራና ቀኝ ያሉት ክፍሎች፣ ባለሦስት ደርብ ናቸው፤ በእያንዳንዱም ደርብ ላይ ሠላሳ ክፍሎች ነበሩ፤ በግንቡም ዙሪያ ግራና ቀኝ ያሉትን እነዚህን ክፍሎች ደግፈው የሚይዙ ተሸካሚዎች ነበሩ፤ ሆኖም ተሸካሚዎቹ ወደ ቤተ መቅደሱ ግንብ ዘልቀው አልገቡም ነበር:: [7]በቤተ መቅደሱ ዙሪያ ያሉት ክፍሎች ስፋት በየደርቡ እየጨመረ የሚሄድ ነው:: በቤተ መቅደሱ ዙሪያ ያለው ሕንጻ አሠራሩ ከታች ወደ ላይ እየሰፋ የሚሄድ

[ሀ]44 ሰብዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *የመዘመራን ክፍሎች ነበሩ፤* ይላል
[ለ]44 ሰብዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *በምሥራቅ* ይላሉ
[ሐ]48 ሰብዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ወጣ ወጣ ያሉት ግንቦች መግቢያ ... ነበሩ* ይላል
[መ]49 ሰብዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ዐሥራ አንድ* ይላል
[ሠ]1 አንድ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጅና ሰብዐ ሊቃናት እንዲሁ ሲሆኑ አብዛኛዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ግን ... *የድንኳኑ ወርድ* ይላሉ

41+1 ቍ23
41+2 2ዜና3+3
41+4 ዘፀ26+33፤ 1ነገ6+20፤ዕብ9+3-8
41+6 1ነገ6+5፤ ሕዝ40+17
41+7 1ነገ6+8

በዚህ ዝርዝር አለመገኘታቸው ግልጽ ነው (43+27፤ 45+17፤ 46+2፡12 ይመ)::

40+46 *የሳዶቅ ልጆች፤* በሳዶቅ ልጆችና በሌዋውያን መካከል ስላለው ልዩነት ሙሉ ትንታኔ የተሰጠበትን የ44+15-31 ማብ ይመ::

40+47 *መሠዊያውም፤* በ43+13-17 ላይ በዝርዝር ተገልጿአል::

40+48 *መተላለፊያ በረንዳ፤* በሰሎሞን ቤተ መቅደስ ካሉ መተላለፊያ በረንዳዎች ጋር ተመሳሳይ ሲሆን፣ እነዚህ ግን በመጠን ተለቅ ያሉ ናቸው (1ነገ 6+3 ይመ)::

40+49 *በየዐምዱ፤* በሰሎሞን ቤተ መቅደስ ውስጥ ያሉት ዐምዶች፣ ያቁምና በለዝ ተብለው ተጠርተዋል (1ነገ 7+21 ይመ)::

41+1 *ወደ መቅደሱ፤* በቤተ መቅደሱ ውስጥ ካሉት ሦስት ዋና ዋና ክፍሎች ትልቅ ወደ ሆነው ማለት ነው፤ በ1ነገ 6+3-5 ዋና አዳራሽ ተብሎ ተጠርቶአል:: የዚህ ቤተ መቅደስ የውጪ ክፍል ከሰሎሞን ቤተ መቅደስ የውጪ ክፍል ጋር ፍጹም ተመሳሳይ ነው (1ነገ6+17 )ይመ::

41+3 *ወደ ውስጥ ገባ፤* ሕዝቅኤል ሳይሆን፣ መልአኩ ብቻ ወደ ቅድስተ ቅዱሳኑ ውስጥ ገባ:: በዘሌ16 ላይ ከሊቀ ካህኑ በስተቀር ማንም ሰው እንዳይገባ ይከለከላል፤ ሊቀ ካህኑም ቢሆን እንኳ መግባት የሚፈቀድለት በዓመት አንድ ጊዜ ብቻ ነው (ዕብ 9+7):: *ወርድ ስድስት ክንድ፤* ወደ ውስጠኛው መቅደስ በዘለቀ ቍጥር፣ በሮቹ እየጠበቡ መሄዳቸውን መረዳት ይቻላል (ዐሥራ አራት ክንድ 40+48፤ ዐሥር ክንድ 41+2)::

41+6 *በእያንዳንዱም ደርብ ላይ ሠላሳ፤* እነዚህ ዘጠና ክፍሎች የካህናት ግምጃ ቤቶች፣ ምናልባትም የዐሥራት

በመሆኑ፣ ወደ ላይ በተሄደ ቍጥር የክፍሎቹ ስፋት እየጨመረ የሚሄድ ነው። በመካከለኛው ደርብ በኩል አድርጎ ከታች ወደ ላይ የተዘረጋም ደረጃ አለ።

[8]ቤተ መቅደሱ ዙሪያውን ከፍ ብሎ የተሠራ መሠረት ያለው መሆኑን አየሁ፤ ይህ ግራና ቀኝ ላሉት ክፍሎች መሠረት ሲሆን፣ ርዝመቱ ስድስት ክንድ ነው፤ ይህም የዘንጉ ቁመት ነበር። [9]በውጭ በኩል ያለው የግራና የቀኙ ክፍሎች ግንብ ውፍረት አምስት ክንድ ነበር፤ ክፍቱ ቦታ በቤተ መቅደሱና [10]በካህናቱ ክፍሎች መካከል ያለ ሲሆን፣ ስፋቱ በቤተ መቅደሱ ዙሪያ ሃያ ክንድ ነበር። [11]ከክፍቱ ቦታ ግራና ቀኝ ወዳሉ ክፍሎች የሚያስገቡ በሮች ነበሩ። አንዱ በሰሜን በኩል ሲሆን፣ ሌላው በር ደግሞ በደቡብ በኩል ነው። ክፍቱን ቦታ ዙሪያውን የሚያገናኘው መሠረት ስፋቱ አምስት ክንድ ነው።

[12]በምዕራብ በኩል ከቤተ መቅደሱ ግቢ ትይዩ የሆነው ሕንጻ ወርድ ሰባ ክንድ ነበር። የሕንጻው ግንብ ውፍረት ዙሪያውን አምስት ክንድ ሲሆን፣ ርዝመቱ ዘጠና ክንድ ነበር።

[13]ከዚያም ቤተ መቅደሱን ለካ፤ ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ ሲሆን፣ የቤተ መቅደሱ ግቢና ሕንጻ ከነግንቡ ደግሞ አንድ መቶ ክንድ ሆነ። [14]በምሥራቅ በኩል የቤተ መቅደሱ ግቢ ስፋት፣ ከቤተ መቅደሱ ፊት ለፊት ያለውን ስፍራ ጨምሮ አንድ መቶ ክንድ ነበር።

[15]ከዚያም ከቤተ መቅደሱ በስተ ጀርባ ከግቢው ትይዩ ያለውን ሕንጻ ለካ፤ ይህም በግራና በቀኝ ያሉትን መተላለፊያዎች የሚጨምር ሲሆን፣ ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ ነበር።

የውጩ መቅደስና የውስጡ መቅደስ ከአደባባዩ ትይዩ ያለው መተላለፊያ በረንዳ፣ [16]እንዲሁም መድረኮቹና ጠበብ ያሉት መስኮቶች፣ በሦስቱም ዙሪያ ያሉት መተላለፊያዎች፣ ከመድረኩ በላይና ራሱ መድረኩም ጭምር ሁሉም በዕንጨት ተለብዶ ነበር። ወለሉ፣ እስከ መስኮቶቹ ያለው ግንብና መስኮቶቹ ተለብደዋል። [17]ከውስጡ መቅደስ መግቢያ በላይ ያለው ውስጡና ውጩ እንዲሁም በውስጡ መቅደስና በውጩ መቅደስ መካከል ያለው ሁሉ ዙሪያውን [18]ኪሩቤልና የዘንባባ ዛፍ ተቀርጸውበት ነበር፤ የዘንባባ ዛፎቹ የተቀረጹት በኪሩብና በኪሩብ መካከል ነበር። እያንዳንዱም ኪሩብ ሁለት ፊት ነበረው፤ [19]የሰው ፊት ያለው ኪሩብ በአንድ በኩል ወዳለው ዘንባባ የዞረ ሲሆን፣ የአንበሳ ፊት ያለውም በሌላ በኩል ወዳለው ዘንባባ ዞሮ ነበር። ሁሉም በቤተ መቅደሱ ዙሪያ ላይ ተቀርጸው ነበር። [20]ከወለሉ አንሥቶ ከመግቢያው በላይ እስካለው ስፍራ ድረስ፣ የውስጡ መቅደስ የውጭ ግድግዳ ላይ ኪሩቤልና የዘንባባ ዛፍ ተቀርጾአል።

[21]የውስጡ መቅደስ በር መቃን ባለ አራት ማእዘን ነበር፤ ከቅድስተ ቅዱሳኑም ፊት ለፊት ያለው በር እንዲሁ ባለ አራት ማእዘን ነበር። [22]ሦስት ክንድ ቁመት፣ ሁለት ክንድ[a] ወርድ፣ ሁለት ክንድ ርዝመት ያለው የዕንጨት መሠዊያ ነበር፤ ማእዘኖቹ፣ መሠረቱና[b] ጐኖቹ ሁሉ ከእንጨት የተሠሩ ነበሩ። ሰውዬውም፣ "ይህች *በእግዚአብሔር* ፊት ያለች ገበታ ናት" አለኝ። [23]የውስጡ መቅደስና ቅድስተ ቅዱሳኑ እያንዳንዳቸው ሁለት ሁለት በር አላቸው፤ [24]እያንዳንዱ በር መካከሉ ላይ በመታጠፊያ የተያያዙ መዝጊያዎች አሉት። [25]በግንቦቹ ላይ እንዳለው ሁሉ በውስጡ መቅደስ በሮችም ላይ ኪሩቤልና የዘንባባ ዛፎች ተቀርጸዋል፤ በመተላለፊያ በረንዳውም ፊት ለፊት የዕንጨት መዝጊያ ተንጠልጥሎአል። [26]በመተላለፊያ በረንዳውም ግራና ቀኝ ግንብ ላይ የዘንባባ ዛፍ ቅርጽ ያለባቸው ጠባብ መስኮቶች ነበሩ። ግራና ቀኝ ያሉት ክፍሎችም በደረጃው በኩል የሚሸፍን ጣሪያ ነበራቸው።

## ለካህናት የተመደቡ ክፍሎች

**42** ከዚያም ያ ሰው በሰሜን በኩል ወዳለው ወደ ውጩ አደባባይ በማምጣት፣ በቤተ መቅደሱ አደባባይ ትይዩና በሰሜን በኩል ባለው ግንብ ትይዩ ወደ አሉት ክፍሎች አመጣኝ። [2]በሩ በሰሜን ትይዩ የሆነው ሕንጻ ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ ወርዱም አምሳ ክንድ ነበር። [3]ከውስጠኛው አደባባይ ሃያ ክንድ ርቀት ላይና በአንጻሩም ከውጩ አደባባይ የንጣፍ ድንጋይ ፊት ለፊት ርቀት ላይ በሦስት ደርቦች ትይዩ የሆኑ ሰገነቶች ነበሩ። [4]ከክፍሎቹ

[a]22 ሰብዓ ሊቃናቱ እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ርዝመቱ ሁለት ወርድ* ይላል

[b]22 ሰብዓ ሊቃናቱ እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ርዝመቱ* ይላል

41፥14 ሕዝ40፥47
41፥15 ሕዝ42፥3
41፥16 ቍ25-26፤ 1ነገ6፥4፡15፤ሕዝ 42፥3
41፥18 ዘፀ37፥7፤ 1ነገ6፥18፡29፤7፥36፤ 2ዜና3፥7፤ሕዝ10፥21
41፥19 ሕዝ10፥14
41፥21 ቍ1
41፥22 ዘፀ25፥23፤ 30፥1፤ሕዝ23፥41
41፥23 ቍ1፤1ነገ 6፥32
41፥24 1ነገ6፥34
41፥26 ቍ15-16፤ ሕዝ40፥16
42፥1 ቍ13፤ዘፀ 27፥9፤ሕዝ40፥17፤ 41፥12-14
42፥3ሕዝ41፥15፡16

ማስቀመጫ ሊሆኑ ይችላሉ (ሚል3፥10 ይመ)።

41፥13 *አንድ መቶ፤* ይህ ቍመቱ፣ ወርዱ፣ ስፋቱ መቶ በመቶ መሆኑ ፍጹምነትን ያሳያል።

41፥16 *ሁሉም በዕንጨት ተለብዶ ነበር፤* በሰሎሞን ቤተ መቅደስ እንዳለው ዐይነት ነው (1ነገ6፥15)።

41፥18 *ኪሩቤል፤* ጠባቂ ሆነው የሚያገለግሉ መላእክት ናቸው (ከዘፍ3፥24 ጋር ያነጻጽሩ)። በዚህ ቍጥር የተገለጹት፣ በም10 ላይ እንደተገለጹት ሳይሆን፣ ሁለት ገጽ ማለትም የሰውና የአንበሳ ፊት ብቻ ያላቸው ናቸው (1ነገ6፥29፡32፡35 ይመ)።

41፥22 *የዕንጨት መሠዊያ፤* ከዋናው ቤተ መቅደስ ውጪ፣ ትልቅ መሠዊያ እንደ ቆመ ሁሉ እንዲሁም (43፥13-17)፣ ከቅድስተ ቅዱሳን ውጭ ትንሽ መሠዊያ ቆሞአል፤ የቆመውም እንደ ምግብ ጠረጴዛ ሊያገለግል ሲሆን፤ ለኅብስተ ገጹ ማስቀመጫ ሳይሆን አይቀርም (ዘፀ25፥30፤ ዘሌ24፥5-9፤ 1ነገ6፥20 ይመ)። በሰሎሞን ቤተ መቅደስም ሆነ በመገናኛው ድንኳን ፊት ለፊት የነበሩትን የዕጣን መሠዊያና መቅረዝን በተመለከተ፣ በዚህኛው ቤተ መቅደስ ውስጥ ስለመገኘታቸው ሕዝቅኤል የገለጸው ነገር የለም፤ እንዲሁም ኪሩብና (1ነገ7፥23) የኪዳኑ ታቦት አልተጠቀሰም።

41፥23 *ሁለት በር፤* የሚታጠፉ በሮች ናቸው፤ ስለዚህም መግቢያው እጅግ ጠባብ ሊሆን ይችላል።

42፥1 *በቤተ መቅደሱ አደባባይ ትይዩ … ወደ አሉት ክፍሎች፤* አገልግሎታቸው ምን እንደ ሆነ ከቍ13-14 ባለው ክፍል ውስጥ ተገልጾአል። ስለ ሰሎሞን ቤተ መቅደስ፣ በ1ነገ6 ላይ ከተገለጸው ጋር እነዚህ ምንም ዐይነት ተመሳሳይነት የላቸውም።

ፊት ለፊት ወርዱ ዐሥር ክንድ፣ ርዝመቱ አንድ መቶ ክንድ[ፀ] የሆነ መተላለፊያ በውስጥ በኩል ነበር። የክፍሎቹም በሮች በሰሜን በኩል ነበሩ። 5የላይኞቹ ክፍሎች ጠበብ ያሉ ናቸው፤ ምክንያቱም ስገነቶቹ ታችና መካከል ላይ ካሉት ከሕንጻው ክፍሎች ይልቅ ሰፋ ያሉ ቦታዎች ይዘውባቸዋልና። 6አደባባዮቹ ዐምዶች ሲኖሯቸው፣ በሦስተኛው ደርብ ላይ ያሉት ክፍሎች ግን ዐምድ የላቸውም። ስለዚህ የወለላቸው ስፋት በታችኛውና በመካከለኛው ደርብ ካሉት ክፍሎች ይልቅ ጠበብ ያለ ነው። 7ከክፍሎቹና፣ ከውጩ አደባባይ ትይዩ የሆነ የውጪ ግንብ አለ፤ ይህም በክፍሎቹ ፊት ለፊት ሆኖ አምሳ ክንድ ይረዝማል። 8ከውጩ አደባባይ ቀጥሎ ያሉት መደዳ ክፍሎች ርዝመት አምሳ ክንድ ሲሆን፣ ከቤተ መቅደሱ አጠገብ ያሉት መደዳ ክፍሎች ርዝመት ደግሞ አንድ መቶ ክንድ ነበር። 9ከውጩ አደባባይ ወደ ውስጥ ሲገባ፣ በስተ ምሥራቅ የታችኛቹ ክፍሎች መግቢያ ይገኛል።

10በደቡብ በኩል[ፈ] የውጩን አደባባይ ግንብ ተከትሎ፣ ከቤተ መቅደሱ አደባባይ ጋር የተያያዙና ከውጩ ግንብ ጋር ትይዩ የሆኑ ክፍሎች አሉ፤ 11ከፊት ለፊታቸውም መተላለፊያ መንገድ አለ። እነዚህ በሰሜን በኩል ካሉት ክፍሎች ጋር ተመሳሳይ ሲሆኑ፣ ርዝመትና ወርዳቸው፣ መውጫና መጠናቸው አንድ ዐይነት ነበር፤ በሰሜን በኩል እንዳሉት በሮች፣ 12በደቡብ በኩል ያሉት ክፍሎች በሮች መጠናቸው ተመሳሳይ ነበር። ከመመላለሻው መነሻ ላይ መግቢያ በር አለ፤ መመለሻውም ፊት ለፊት ካለው ወደ ምሥራቅ ከሚያመራው ግንብ ጋር ተጓዳኝ ነው።

13ከዚያም እንዲህ አለኝ፤ “ከቤተ መቅደሱ አደባባይ ፊት ለፊት ያሉት የሰሜኑና የደቡቡ ክፍሎች የካህናቱ ሲሆኑ፣ እነዚህም *በእግዚአብሔር ፊት የሚቀርቡት ካህናት* እጅግ የተቀደሱትን ቍርባኖች የሚበሉባቸው ናቸው። በዚያም እጅግ የተቀደሱትን ቍርባኖች ማለት የእህሉን ቍርባን፣ የኀጢአቱን ቍርባን፣ የበደሉን ቍርባን ያስቀምጣሉ፤ ቦታው ቅዱስ ነውና። 14ካህናቱ አንድ ጊዜ ወደ ተቀደሰው ቦታ ከገቡ በኋላ፣ ያገለገሉበትን ልብስ ሳያወልቁ ወደ ውጩ አደባባይ መውጣት አይችሉም፤ የተቀደሰ ነውና፤ ወደ ሕዝቡ ቦታ ከመምጣታቸው በፊት ሌላውን ልብሳቸውን መልበስ አለባቸው።”

15በቤተ መቅደሱ ውስጥ ያለውን ስፍራ ለክቶ ከጨረሰ በኋላ፣ በምሥራቅ በር በኩል ወደ ውጩ አወጣኝ፤ በዙሪያው ያለውንም ስፍራ ሁሉ ለካ፤ 16በምሥራቅ ያለውንም በመለኪያው ዘንግ ለካ፤ አምስት መቶ ክንድ[ፐ] ሆነ። 17ሰሜኑንም ለካ፤ በመለኪያው ዘንግ አምስት መቶ ክንድ[ሀ] ሆነ። 18ደቡቡንም ለካ፤ በመለኪያው ዘንግ አምስት መቶ ክንድ ሆነ። 19ከዚያም ወደ ምዕራብ ጐን ዞሮ ለካ፤ በመለኪያው ዘንግ አምስት መቶ ክንድ ሆነ። 20ስለዚህ በአራቱም ማእዘን ለካው፤ የተቀደሰውን ስፍራ ከሌላው የሚለይ በዙሪያው ግንብ ነበረ፤ የግንቡም ርዝመት አምስት መቶ ክንድ ሲሆን፣ ወርዱ አምስት መቶ ክንድ ነበር።

## የእግዚአብሔር ክብር ወደ ቤተ መቅደሱ መመለስ

**43** ከዚያም ያ ሰው ለምሥራቅ ትይዩ ወደ ሆነው በር አመጣኝ፤ 2እኔም የእስራኤል አምላክ ክብር ከምሥራቅ ሲመጣ አየሁ፤ ድምፁ እንደ ባሕር ሞገድ ድምፅ ነበር፤ ምድሪቱም ከክብሩ የተነሣ ታበራ ነበር። 3ያየሁትም ራእይ ከተማዪቱን ለማጥፋት በመጣ ጊዜ ያየሁትን ራእይ የሚመስልና እንዲሁም በኮቦር ወንዝ ካየሁት ራእይ ጋር የሚመሳሰል ነበር፤ እኔም በግንባሬ ተደፋሁ። 4*የእግዚአብሔር* ክብር ለምሥራቅ ትይዩ በሆነው በር ወደ ቤተ መቅደሱ ገባ። 5ከዚያም መንፈስ አነሣኝ፤ ወደ ውስጠኛው አደባባይ አመጣኝ፤ *የእግዚአብሔርም* ክብር ቤተ መቅደሱን ሞላው።

[ፀ]4 ሰብዓ ሊቃናቱና ሱርስቱ እንዲሁ ሲሆኑ ዕብራይስጡ ግን … *አንድ ክንድ* ይላል

[ፈ]10 ሰብዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *በስተ ምሥራቅ* ይላል

[ፐ]16 ከሰብዓ ሊቃናት ቍ17ን ይመ፤ ዕብራይስጡ ግን *ዘንጎች* ይለዋል፤ እንዲሁም ቍ18 እና 19

[ሀ]17 ሰብዓ ሊቃናቱም እንዲሁ ሲሆን፣ ዕብራይስጡ ግን *ዘንጎች* ይላል

42+4 ሕዝ46+19
42+9 ሕዝ44+5፤ 46+19
42+10 ቍ1፤ሕዝ 41+12-14
42+13 ቍ1፤ዘፀ 29+31፤ዘሌ6+29፤7+6፤10+12-13፡17፤ 14+13፤ዘኍ18+9-10፤ኤር41+5፤ሕዝ40+46፤41+12-14
42+14 ዘፀ29+9፤ ዘሌ8+7-9፤16+23፤ ሕዝ44+19
42+15 ሕዝ43+1
42+20 ሕዝ22+26፤ 40+5፤43+12፤45+2፤ ዘካ2+5፤ራእ21+16
43+1 1ዜና9+18፤ ሕዝ8+16፤42+15፤ 44+1
43+2 መዝ18+4፤ ኢሳ6+3፤ራእ1+15፤ 18+1፤21+11
43+4 ሕዝ1+28፤ ሕዝ10+19፤44+2
43+5 ዘፀ16+7፤ ኢሳ6+4፤ሕዝ3+12፤ 11+24

42+13 *በእግዚአብሔር ፊት የሚቀርቡት ካህናት፣* የሳዶቅ ልጆች ማለት ነው (40+6 እና የ44+15 ማብ ይመ)። *እጅግ የተቀደሱትን ቍርባኖች የሚበሉባቸው፣* ካህናት ራሳቸውን በከፊል ለመደገፍ እንዲችሉ፣ የተወሰኑ መስዋዕቶችን እንዲበሉ ይፈቀድላቸው ነበር (ዘሌ 2+3፤ 5+13፤ 6+16፡26፡29፤ 7+6፡10 ይመ)።

*42+20፤ ርዝመት አምስት መቶ ክንድ ሲሆን፣ ወርዱ አምስት መቶ ክንድ ነበር፤* የቤተ መቅደሱ ወርድና ርዝመት እኩል መሆኑ ለአጠቃላዩ ስፋት ልዩ ውበትን ያጐናጽፈዋል።

43+2 *እኔም … ክብር አየሁ፤* ከም40–48 ላለው ክፍል ዐቢይ ሐሳብ ነው፤ ቤተ መቅደሱ የተዘጋጀውም ለዚህ ጕዳይ ነበር፤ ቀጥሎ ላለው ሁኔታም መነሻው ይኸው ነው። *ከምሥራቅ ሲመጣ፤* እግዚአብሔር ከቤተ መቅደሱ ወጥቶ በሄደ ጊዜ፣ ሕዝቅኤል የተመለከተው አቅጣጫ ይህ ነው (11+23 ይመ)። በሕዝቅኤል መጽሐፍ ውስጥ የእግዚአብሔር ክብር በገሃድ ይታይ ነበር (ቍ4-5፤ 3+23፤ 9+3፤ 10+4፡18፤ 44+4 ይመ)። *እንደ ባሕር ሞገድ ድምፅ፤* ሕዝቅኤል ራእይ እንዳየ ሁሉ፣ ድምፅም ሰምቶአል፤ ለማነጻጸርም 1+24፤ ራእ1+15፤ 14+2፤ 19+6 ይመ። *ምድሪቱም ከክብሩ የተነሣ ታበራ ነበር፤* የእግዚአብሔር ክብር በተገለጠ ጊዜ እንደ ብሩህ ጸዳል ሆኖ ይታያል (10+4፤ ሉቃ 2+9፤ ራእ21+11፡23 ይመ)።

43+3 *ከተማዪቱን ለማጥፋት በመጣ ጊዜ፤* ም9 ይመ። *ያየሁትን ራእይ የሚመስል፤* የተለየ ከመሆኑ የተነሣ፣ ሕያዋን ፍጡራኑም ሆኑ መንኰራኵሮቹ፣ በዚህ ቍጥር ላይ አልተገለጹም። *በኮቦር ወንዝ፤* ም1 ይመ። *በግንባሬ ተደፋሁ፤* 1+28፤ 3+23፤ 9+8፤ 11+13፤ 44+4 ይመ።

43+4 *ለምሥራቅ ትይዩ በሆነው በር፤* የቍ2 ማብ ይመ።

43+5 *መንፈስ አነሣኝ፤* እግዚአብሔር እየቀረበ በመጣ ጊዜ፣ የመሪው መልአክ ተግባር በእግዚአብሔር መንፈስ ተተካ። ሕዝቅኤልም ወደ ቤተ መቅደሱ ውስጥ ሳይሆን፣ ወደ ውስጠኛው አደባባይ ተወሰደ (ከ3+14፤ 8+3፤ 11+1፡24 ጋር ያነጻጽሩ)። *ቤተ መቅደሱን ሞላው፤* የሰሎሞን ቤተ መቅደስ በተቀደሰ ጊዜ እንደ ሆነው ማለት ነው። (1ነገ8+11፤ ዘፀ40+34-35፤ ኢሳ 6+4 ይመ)።

[6]ያ ሰው በአጠገቤ ቆሞ ሳለ፣ ከቤተ መቅደሱ ውስጥ ሲናገረኝ ሰማሁ፤ [7]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ “የሰው ልጅ ሆይ፤ ይህ የዙፋኔ *መቀመጫ የእግሬም ጫማ ማሳረፊያ* ነው፤ በእስራኤላውያን መካከል ለዘላለም የምኖርበትም ስፍራ ነው። የእስራኤል ቤትም ሆኑ ነገሥታታቸው በአመንዝራነታቸውና[ሀ] በማምለኪያ ኰረብታቸው ላይ በሚያመልኳቸው፣ ሕይወት በሌላቸው በነገሥታታቸው ጣዖታት[ለ] ከእንግዲህ ቅዱስ ስሜን አያረክሱም። [8]በእኔና በጣዖታቱ መካከል ግንብ ብቻ ሲቀር፣ መድረኮቻቸውን ከመድረኬ አጠገብ፣ መቃኖቻቸውን ከመቃኖቼ አጠገብ በማድረግ፣ በአስጸያፊ ድርጊታቸው ቅዱስ ስሜን አረከሱ፤ ስለዚህ በቍጣዬ አጠፋኋቸው። [9]ከእንግዲህ አመንዝራነታቸውንና ሕይወት የሌላቸውን የንጉሦቻቸውን ጣዖታት ከእኔ ዘንድ ያርቁ፤ እኔም በመካከላቸው ለዘላለም እኖራለሁ።

[10]“የሰው ልጅ ሆይ፤ ስለ ኀጢአታቸው ያፍሩ ዘንድ፣ ለእስራኤል ሕዝብ ቤተ መቅደሱን አሳያቸው፤ ንድፉንም ያስተውሉ፤ [11]ስላደረጉት ነገር ሁሉ ኀፍረት የሚሰማቸው ከሆነ፣ የቤተ መቅደሱን ንድፍ እንዲያውቁት አድርግ፤ ይኸውም አሠራሩን፣ መውጫና መግቢያውን፣ አጠቃላይ ንድፉን፣ ሥርዐቱንና ሕጉን ሁሉ[ሐ] ነው። ንድፉንና ሥርዐቱን እንዲጠብቁና እንዲከተሉ እነዚህን ሁሉ እነርሱ ባሉበት ጻፋቸው።

[12]“የቤተ መቅደሱ ሕግ ይህ ነው፤ በተራራው ጫፍ አካባቢ ያለው ስፍራ ሁሉ እጅግ የተቀደሰ ይሆናል። የቤተ መቅደሱም ሕግ ይኸው ነው።

43፥7 ዘሌ26፥30፤ ኤር3፥17፤ ሕዝ20፥29፡39፤ 37፥23
43፥9 ሕዝ37፥26-28
43፥10 ሕዝ16፥61
43፥11 ሕዝ44፥5
43፥12 ሕዝ17፥22፤ 42፥20
43፥13 ዘፀ20፥24፤ 2ዜና4፥1
43፥15 ዘፀ27፥2፤ ኢሳ29፥2
43፥16 ራእ21፥16
43፥17 ቍ20፤ ዘፀ20፥26፤27፥1፤ ሕዝ 45፥19
43፥18 ዘፀ40፥29፤ ዘሌ1፥5፡11፤ ዕብ 9፥21-22
43፥19 ዘሌ4፥3፤ ዘኍ16፥40፤ 2ሳሙ8፥17፤ ዕዝ7፥2፤ሕዝ40፥46

## የቤተ መቅደሱ መሠዊያ

[13]“የመሠዊያው ልክ በረጅም ክንድ ይህ ነው፤ ይኸውም ክንድ ከስንዝር ማለት ነው፤ በዩ አንድ ክንድ ጥልቀት፣ አንድ ክንድ ወርድ ያለው ሲሆን፣ ዙሪያው አንድ ስንዝር ጠርዝ አለው፤ የመሠዊያውም ከፍታ ይህ ነው፤ [14]ከቦዩ መሠረት አንሥቶ እስከ ታችኛው ዕርከን ድረስ ሁለት ክንድ ቁመት፣ ሁለት ክንድ ወርድ ያለው ሲሆን፣ ከትንሹ ዕርከን አንሥቶ እስከ ትልቁ ዕርከን ድረስ ደግሞ አራት ክንድ ቁመት፣ አንድ ክንድ ወርድ አለው። [15]የመሠዊያው ምድጃ ከፍታው አራት ክንድ ሲሆን፣ ከምድጃው ወጣ ወጣ ያሉ አራት ቀንዶች አሉ። [16]የመሠዊያው ምድጃ እኩል በእኩል ሲሆን፣ ርዝመቱ ዐሥራ ሁለት ክንድ፣ ወርዱም ዐሥራ ሁለት ክንድ ነው። [17]ላይኛው ዕርከንም እንዲሁ እኩል በእኩል ሆኖ ዐሥራ አራት ክንድ ርዝመትና ዐሥራ አራት ክንድ ወርድ አለው፤ ግማሽ ክንድ ጠርዝና ዙሪያውን በሙሉ አንድ ክንድ የሆነ ቦይ ነበረው። የመሠዊያው ደረጃዎችም በምሥራቅ ትይዩ ናቸው።”

[18]ከዚያም እንዲህ አለኝ፤ “የሰው ልጅ ሆይ፤ ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ መሠዊያው ተሠርቶ፣ የሚቃጠል መሥዋዕት በሚሠዋበትና በመሠዊያው ላይ ደም በሚረጭበት ጊዜ ሥርዐቶቹ እነዚህ ናቸው፤ “[19]በፊቴ ቀርበው ለሚያገለግሉኝ ካህናት፣ ለሌዋውያኑ ለሳዶቅ ቤተ ሰብ የኀጢአት

[ሀ] 7 ወይም *መንፈሳዊ ግልሙትናቸውን፤* እንዲሁም ቍ9
[ለ] 7 ወይም *ሬሳ* እንዲሁም ቍ 9
[ሐ] 11 አንዳንድ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆችና ሰብዐ ሊቃናት እንዲሁ ሲሆኑ አብዛኞዎቹ የዕብራይስጥ የጥንት ቅጆች ግን *ሥርዓቶቹንና የራሱን ንድፎች ሁሉ ይላሉ*

43፥6 *ሲናገረኝ፤* ከታላቅ አክብሮትና ፍርሀት የተነሣ፣ የእግዚአብሔርን ስም ላለመጥራት የገባ ነው።

43፥7 *የዙፋኔ መቀመጫ፤* ኢሳ6፥1፤ ኤር3፥17 ይመ። *የእግሬም ጫማ ማሳረፊያ፤* 1ዜና28፥2፤ መዝ99፥5፤ 132፥7፤ ኢሳ60፥13፤ ሰቆ 2፥1 ይመ። *በእስራኤላውያን መካከል ለዘላለም የምኖርበት፤* በ37፥26-28 የተሰጠውን የተስፋ ቃል የሚያጠናክር ነው (ቍ9፤ 1ነገ6፥13፤ ዘካ2፥11 ይመ)። *በአመንዝራነታቸው፤* በአማራጭ ትርጕሙ እንደተገለጸው፣ የቃሉ ትርጕም ምናልባት በቤተ ጣዖት ሥርዐተ አምልኮ ወቅት የሚፈጸመው ዝሙት ወይም እግዚአብሔርን ከመከተል ወደ ጣዖት አምልኮ መመለስን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (የ16፥15 ማብ ይመ)። *ሕይወት በሌላቸው … ጣዖታት፤* በአማራጭ ትርጕሙ እንደተገለጸው፣ ይህ የሚያመለክተው ጣዖቶችን ወይም የቀድሞዎችን ነገሥታት መታሰቢያ ሐውልቶች ወይም መቃብሮቻቸውን ሊሆን ይችላል። ቤተ መቅደሱ ባለበት አካባቢ ማለትም ለሕዝቅኤል እጅግ ቅርብ በሆነ ስፍራ ላይ ዐሥራ አራት የይሁዳ ነገሥታት መቃብር ይገኝ ነበር (2ነገ21፥18፡26፤ 23፥30 ይመ)።

43፥8 *መድረኮቻቸውን ከመድረኬ አጠገብ፤* የሰሎሞን ቤተ መቅደስ ራሱ ንጉሥ ሰሎሞን በግል ባሠራቸው ሕንጻዎች የተከበበ ነበር (1ነገ7፥1-12)። በእግዚአብሔር ቅዱስ ቤተ መቅደስና በሌላው ስፍራ መካከል ያለውን ልዩነት ማመልከት፣ የሕዝቅኤል መጽሐፍ ማዕከላዊ ሐሳብ ነው (ቍ12፤ 44፥23 ይመ)። *ስለዚህ … አጠፋኋቸው፤* በሕዝቅኤል መጽሐፍ እንደተገለጸው፣ የሕዝቡና ነገሥታቶቻቸው በእምነታቸው ጸንተው አለመገኘታቸው ለመጥፊያቸው ምክንያት ነበር (5፥11፤ 18፥10-12 በተለይም 22፥1-15 ይመ)።

43፥12 *ሕግ ይህ ነው፤* ከም40-42 ያሉትን ዝርዝር ሐሳቦች ያገናዘበ ነው።

43፥13 *መሠዊያው፤* በግልጽ ባይሆንም በ40፥47 ላይ ተገልጾአል፣ በእዚህ ቍጥር ላይም በዝርዝር ቀርቦአል። ከምን እንደተሠራ ባይገለጽም እንኳ፣ ምናልባት ከተወቀሩ ድንጋዮች ሊሆን ይችላል። በዘፀ20፥24-26 ላይ እንደተጠቀሰው መሠዊያ ሊሠራ የሚገባው ከዐፈር ብቻ ነው፤ ሆኖም ግን መሠዊያዎችን ከተወቀረ ድንጋይ መሥራት ደግሞ ፈጽሞ የተከለከለ ነው (የዘፀ 20፥24-25 ማብ ይመ)። ሰሎሞን ያሠራው መሠዊያ ከናስ የተሠራ ነው (1ነገ 8፥64)፤ ከሰሎሞን መሠዊያ እጅግ የሚበልጠው የሕዝቅኤል መሠዊያ ቁመቱ ስድስት ሜትር ያህል ሲሆን፣ እንደ ግብፅ ፒራሚድ ወይም እንደ ባቢሎን ዚጉራት መጠናቸው እያነሰ በሚሄድ ሦስት ጥርብ ድንጋዮች የተሠራ ነው፤ “ታችኛው ዕርከን” (ቍ14) ቁመቱ አንድ ሜትር ሲሆን፣ ትልቍ ዕርከን ደግሞ ቁመቱ ሁለት ሜትር (ቍ14) ነው፣ እንዲሁም የመሠዊያው ምድጃ (ቍ15) ቁመቱም ሁለት ሜትር ነው።

43፥15 *የመሠዊያው ምድጃ፤* ይህ ሐረግ በዕብራይስጥ፣ በብሉይ ኪዳን ውስጥ ነው የሚገኘው፤ ትርጕሙም? “የእግዚአብሔር ተራራ” ወይም “የአምላክ አንበሳ” ማለት ሲሆን፣ በኢሳ 29፥1-2 ላይ ከተጠቀሰው ጋር ግን ይህ ለየት ያለ ትርጕም አለው። *አራት ቀንዶች፤* ከድንጋይ የተቀረጹና በመሠዊያው ምድጃ አራት ማእዘናት ላይ ያሉ ናቸው። በጥንት ጊዜ እነዚህ የመሠዊያ ቀንዶች፣ በወንጀል ለሚፈለግ ሰው መሸሸ፣ መጠጊያና መማጸኛ በመሆን ያገለግሉ ነበር (ዘፀ21፥12-14፤ 1ነገ1፥50-51፤ 2፥28-29 ይመ)።

43፥17 *የመሠዊያው ደረጃዎች፤* እነዚህ በዘፀ20፥26 ላይ እንዳይሠሩ የተከለከሉ ቢሆንም፣ እዚህ ላይ ግን መሠዊያው ትልቅ ስለሆነ የደረጃዎቹ መኖር አስፈላጊ ነበር (የቍ13 ማብ ይመ)።

43፥18 *የሚቃጠል መሥዋዕት፤* የ40፥39 ማብ ይመ። *ደም በሚረጭበት ጊዜ፤* ዘፀ29፥16፤ ዘሌ4፥6፤ 5፥9 ይመ።

43፥19 *የኀጢአት መሥዋዕት፤* በሰው ኀጢአት የተበከለውን መሠዊያ ለማንጻት ነው (የ40፥39 ማብ ይመ)። *ለሳዶቅ ቤተ ሰብ፤* የ44፥15 ማብ ይመ።

መሥዋዕት የሚሆን አንድ ወይፈን ስጥ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*:: [20]ከደሙም ጥቂት ወስደህ፣ በመሠዊያው አራት ቀንዶች፣ በላይኛው ዕርከን አራት ጐኖች ላይ እንዲሁም በጠርዙ ዙሪያ ሁሉ ታደርጋለህ፤ በዚህ ሁኔታ መሠዊያውን ታነጻለህ፤ ታስተሰርይለታለህም:: [21]ወይፈኑን ስለ ኀጢአት መሥዋዕት ወስደህ፣ በቤተ መቅደሱ አካባቢ ከመቅደሱ ውጪ ለዚሁ ተብሎ በተመደበው ስፍራ ታቃጥለዋለህ::

[22]“በሁለተኛው ቀን እንከን የሌለበት ተባት ፍየል ወስደህ ለኀጢአት መሥዋዕት ታቀርባለህ፤ መሠዊያው በወይፈኑ እንደ ነጻ ሁሉ፣ በዚህም መንጻት አለበት:: [23]ማንጻቱን ከፈጸምህ በኋላ፣ ከመንጋው እንከን የሌለባቸውን አንድ ወይፈንና አንድ አውራ በግ ታቀርባለህ:: [24]*በእግዚአብሔር* ፊት ታቀርባቸዋለህ፤ ካህናቱ ጨው ይነሰንሱባቸዋል፤ *ለእግዚአብሔርም* የሚቃጠል መሥዋዕት አድርገው ያቀርቧቸዋል::

[25]“በየዕለቱ ለሰባት ቀን ተባት ፍየል ለኀጢአት መሥዋዕት ታቀርባለህ፤ [26]ሰባት ቀን ለመሠዊያው ያስተሰርዩለታል፤ ያነጹታልም፤ እንዲህም አድርገው ይቀድሱታል:: [27]እነዚህ ቀኖች ካለፉ በኋላም፣ ከስምንተኛው ቀን ጀምሮ ካህናቱ የሚቃጠለውን መሥዋዕታችሁንና የኅብረት መሥዋዕታችሁን[*] በመሠዊያው ላይ ያቀርባሉ:: ከዚያም እኔ እቀበላችኋለሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*::”

## ገዢው፣ ሌዋውያኑ፣ ካህናቱ

**44** ከዚያም ያ ሰው ለምሥራቅ ትይዩ ወደ ሆነው በስተ ውጪ ወዳለው ወደ መቅደሱ በር መልሶ አመጣኝ፤ ተዘግቶም ነበር:: [2]*እግዚአብሔር* እንዲህ አለኝ፤ “ይህ በር እንደ ተዘጋ ይኖራል፤ መከፈት የለበትም፤ ማንም አይገባበትም፤ የእስራኤል አምላክ *እግዚአብሔር* ገብቶበታልና፤ ተዘግቶ ይኖራል:: [3]*በእግዚአብሔር* ፊት ይበላ ዘንድ በመግቢያው በር ገብቶ ውስጥ ሊቀመጥ የሚችለው ገዢ ራሱ ብቻ ነው፤ በመግቢያው መተላለፊያ በረንዳ እንደ ገባ መውጣትም የሚችለው በዚያው ነው::”

[4]ከዚያም ያ ሰው በሰሜኑ በር በኩል ወደ ቤተ መቅደሱ ፊት ለፊት አመጣኝ፤ እኔም ተመለከትሁ፤ *የእግዚአብሔርም* ክብር *የእግዚአብሔርን* ቤተ መቅደስ ሞልቶት አየሁ፤ በግንባሬም ተደፋሁ::

[5]*እግዚአብሔር* እንዲህ አለኝ፤ “የሰው ልጅ ሆይ፤ ስለ *እግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ሥርዐት የምነግርህን ሁሉ በጥንቃቄ አስተውል፤ በሚገባ አድምጥ፤ ልብም በለው:: የቤተ መቅደሱን መግቢያና የመቅደሱን መውጫዎች ሁሉ አስተውል፤ [6]ለዐመፀኛው የእስራኤል ቤት እንዲህ በል፤ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ “የእስራኤል ቤት ሆይ፤ አስጸያፊ ሥራችሁ ከእንግዲህ ያብቃ! [7]ከአስጸያፊ ሥራችሁም ሌላ ምግብ፣ ስብና ደም ስታቀርቡ ልባቸውንና ሥጋቸውን ያልተገረዙትን እንግዶች ወደ መቅደሴ በማስገባት ቤተ መቅደሴን አረከሳችሁ፤ ቃል ኪዳኔንም አፈረሳችሁ:: [8]እናንተ ራሳችሁ ማድረግ የሚገባችሁን ቅዱሳት ሥርዐቶቼን በመፈጸም ፈንታ ባዕዳንን በኀላፊነት በመቅደሴ አስቀመጣችሁ:: [9]ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ በልቡና በሥጋው ያልተገረዘ ባዕድ በእስራኤላውያን መካከል የሚኖር ቢሆንም እንኳ ወደ መቅደሴ አይግባ::

[10]‘ “እስራኤል እኔን ከመከተል በራቀ ጊዜ፣ ከእኔ የራቁትና ጣዖቶቻቸውን በመከተል የተቅበዘበዙት ሌዋውያን የኀጢአታቸውን ዕዳ ይሸከማሉ:: [11]የቤተ መቅደሱ በር ኀላፊ በመሆንና በእርሱም ውስጥ በማገልገል፣ መቅደሴን ሊያገለግሉ ይችላሉ፤ የሚቃጠለውን መሥዋዕት ዐርደው ስለ ሕዝቡ

[*]27 በትውፊት *የድነት መሥዋዕት* ይባላል

43+20 ቍ17፤ ዘሌ4+7፤16+19
43+21 ዘፀ29+14፤ ዕብ13+11
43+23 ዘፀ29+1፤ ዘሌ22+20
43+24 ዘሌ2+13፤ ማር9+49-50
43+25 ዘፀ29+37፤ ዘሌ8+33
43+27 ዘፀ32+6፤ ዘሌ9+1፤17+5፤ኢሳ 60+7
44+1 ሕዝ43+1
44+2 ሕዝ43+4-5
44+3 ዘፀ24+9-11፤ ሕዝ46+2:8
44+4 ኢሳ6+4፤ ሕዝ 10+4፤40+35፤ ዳን 8+17፤ራእ15+8
44+5 ሕዝ40+4፤ 42+9፤43+10-11
44+6 ሕዝ3+9
44+7 ዘፍ17+14፤ ዘፀ12+48፤ዘሌ22+25፤ 26+41
44+8 ዘኍ18+7፤ ዘሌ22+2
44+9 ኢዩ3+17፤ ዘካ14+21
44+10 ዘኍ18+23፤ መዝ95+10
44+11 ዘኍ3+5-37፤ 16+9፤1ዜና26+12 -19፤2ዜና29+34

43+21 *ከመቅደሱ ውጪ፤* በዘፀ29+14፤ ዘሌ4+12:21፤ 8+17፤ 9+11፤ 16+27 በተገለጸው መሠረት ማለት ነው:: ይህ ድርጊት ክርስቶስ ራሱን ፍጹም መሥዋዕትነት አድርጎ ከአቀረበባቸው ሁኔታዎች ለአንዱ ጥላ ነው (ዕብ13+11-13 ይመ)::

43+22 *መንጻት አለበት፤* ደም በመርጨት ማለት ነው (ቍ20 ይመ)::

43+27 *የኅብረት መሥዋዕታችሁን፤* ሕዝቡ ሥጋ በመብላት ለሚያከብረው የኅብረት መሥዋዕት በዓል፣ መሠዊያው ሰባት ቀን በሚቃጠል መሥዋዕትና በኀጢአት መሥዋዕት ከተቀደሰ በኋላ ዝግጁ ይሆናል (ዘሌ3 ይመ)::

44+2 *እንደ ተዘጋ ይኖራል፤* ለዚህ የተሰጠው ምክንያት እግዚአብሔር በምሥራቅ በር ስለ ገባና (43+1-2)፣ ስፍራውንም ቅዱስ ስላደረገው ነው:: ሌላው ምክንያት ሊሆን የሚችለው ደግሞ፣ እንደ በፊቱ እግዚአብሔር መቅደሱን ትቶ ስለማይወጣ (10+19፤ 11+23) ለፀሓይ የሚደረገው አምልኮ ሊከናወን ስለማይችል ነው (8+16 ይመ):: ዛሬ ወርቃማው በር ተብሎ የሚጠራው የምሥራቁ በር አካባቢ በሙስሊሞች የተቀደሰ ስፍራ ነው፤ ይህ በኢየሩሳሌም የሚገኘው በር ታሽጓል፤ ይህም የሆነበት ምክንያት፣ ሌላ ‘አምልኮ እንዳይካሄድ ወይም ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ትውፊት ስላለ ሊሆን ይችላል::

44+3 *ይበላ ዘንድ፤* ምናልባት ከኅብረት መሥዋዕቱ የራሱን ድርሻ ማለቱ ይሆናል (ዘሌ7+15፤ ዘዳ12+7 ይመ፤ በተጨማሪም ሕዝ43+27 እና ማብ ይመ):: ይህ ክብር ለገዥው ቢሰጠውም፣ በሥርዐቱ ላይ ከሚደረጉትና የካህናቱ ብቻ ድርሻ ከሆኑት ነገሮች ግን አልተሰጡትም (2ዜና26+16-20 ይመ):: *ገዢው፤* ይህ ገዢ ለመጀመሪያ ጊዜ ከም40-48 ባለው ክፍል ውስጥ የተጠቀሰው እዚህ ነው (34+24 እና ማብ ይመ):: *መተላለፊያ በረንዳ፤* በውጪው አደባባይ ውስጥ በኩል ማለት ነው::

44+7 *ልባቸውንና ... ያልተገረዙትን፤* መንፈሳዊ ብቃት የሌላቸውን ማለት ነው::

44+9 *ያልተገረዘ ባዕድ ... ወደ መቅደሴ አይግባ፤* ነህምያ አሞናዊውን ጦቢያን በዚህ ትእዛዝ መሠረት ከቤተ መቅደስ አስወጥቶታል (ነህ13+8፤ ነህ2+10፤ ዘዳ23+3 ይመ):: ይሁን እንጂ፣ መጻተኞችም እንደ እስራኤላውያን የሚቈጠሩባቸው ሁኔታዎች አሏቸው (47+22 ይመ)::

44+10 *ሌዋውያን፤* ከሌዊ ነገድ የተወለዱ እነዚህ ሌዋውያን፣ ከጥንት ጀምሮ ካህናት በመሆን ያገለግሉ ነበር (ዘዳ33+8-11፤ መሳ17+13 ይመ):: *እስራኤል እኔን ከመከተል በራቀ ጊዜ፤* ይህ አባባል የሚመለከተው እስራኤል በነገሥታት ትገዛ በነበረበት በመጨረሻው ዘመን ነው፤ በዚህ ጊዜም፣ ሕዝቡ ጣዖትን በማምለኩ ሕዝቅኤል በተደጋጋሚ ይነቅፋቸው ነበር (6+3-6፤ 14+3-11፤ 16+18-21፤ 23+36-49፤ 36+17-18፤ 37+23 ይመ)::

44+11 *በፊታቸው ሊቆሙ፤* በእግዚአብሔር ፊት ከመቆም ጋር ያነጻጽሩ (ቍ15)፤ ሌዋውያን በወቅቱ የከበረ ቦታ ነበራቸው

ሊሠዉ፣ በፊታቸው ሊቆሙና ሊያገለግሏቸው ይችላሉ:: [12]ነገር ግን ሕዝቡን በጣዖቶቻቸው ፊት ስላገለገሏቸውና የእስራኤል ቤት በኀጢአት እንዲወድቅ ስላደረጉ፣ ስለዚህ የኀጢአታቸውን ዋጋ መቀበል እንዳለባቸው እጄን አንሥቼ ምያለሁ፤ ይላል *ጌታ እግዚአብሔር*:: [13]እንደ ካህናት ያገለግሉኝ ዘንድ ወደ እኔ አይቀርቡም፤ ወይም ቅዱስ ወደ ሆነው ነገሬ ሁሉ፣ ወይም እጅግ ወደ ተቀደሱ መሥዋዕቶቼ አይቀርቡም፤ የአስጸያፊ ድርጊታቸውን ኀፍረት ይሸከማሉ:: [14]ያም ሆኖ የቤተ መቅደሱን ሥራ በኀላፊነት እንዲሠሩ፣ በውስጡ የሚከናወኑትንም ሥራዎች ሁሉ እንዲቈጣጠሩ አደርጋቸዋለሁ::

[15]“ነገር ግን እስራኤላውያን ከመንገዴ ስተው በወጡ ጊዜ፣ የመቅደሴን ሥራ በታማኝነት ያከናወኑት የሳዶቅ ዘርና ሌዋውያን የሆኑት፣ በፊቴ ቀርበው ያገለግሉኛል፤ በፊቴ ቆመው የስብና የደም መሥዋዕት ያቀርቡልኛል፤ ይላል *ጌታ እግዚአብሔር*:: [16]እነርሱ ብቻ ወደ መቅደሴ ይገባሉ፤ እነርሱ ብቻ በፊቴ ሊያገለግሉ፣ ሥርዐቴንም ሊፈጽሙና ወደ ገበታዬ ሊቀርቡ ይችላሉ::

[17]“ወደ ውስጠኛው አደባባይ በሮች ሲገቡ፣ የበፍታ ፈትል ይልበሱ፤ በውስጠኛው አደባባይ በሮችም ሆነ በቤተ መቅደሱ ውስጥ ሲያገለግሉ፣ ከበግ ጠጕር የተሠራ ልብስ አይልበሱ:: [18]በራሳቸው ላይ ከበፍታ ፈትል የተሠራ ጥምጥም ያድርጉ፤ እንዲሁም ከበፍታ ፈትል የተሠራ ሱሪ በወገባቸው ላይ ይታጠቁ፤ እንዲያልባቸው የሚያደርግ ማንኛውንም ልብስ አይልበሱ:: [19]ሕዝቡ ወዳለበት ወደ ውጭ አደባባይ ሲወጡ፣ ሲያገለግሉበት የነበረውን ልብስ አውልቀው በተቀደሱት ክፍሎች በመተው ሌሎች ልብሶችን ይልበሱ፤ ይኸውም ሕዝቡን በልብሳቸው እንዳይቀድሱ ነው::

[20]“የራሳቸውን ጠጕር አይላጩት፤ ወይም አያርዝሙት፤ ነገር ግን ይከርክሙት:: [21]ማንኛውም ካህን ወደ ውስጠኛው አደባባይ በሚገባበት ጊዜ የወይን ጠጅ አይጠጣ:: [22]መበለቶችን ወይም ፈት ሴቶችን አያግቡ፤ ነገር ግን ከእስራኤል ዘር የሆኑ ድንግሎችን ወይም የካህናት ሚስቶች የነበሩትን መበለቶች ማግባት ይችላሉ:: [23]በተቀደሰውና ባልተቀደሰው መካከል ያለውን ልዩነት ለሕዝቤ ያስተምሩ፤ የረከሰውንና ያልረከሰውን እንዴት እንደሚለዩም ያሳዩአቸው::

[24]“በማንኛውም ክርክር ካህናት ዳኞች ሆነው ያገልግሉ፤ በሥርዐቴም መሠረት ይወስኑ:: የተለዩ በዓላቴን የሚመለከቱ ሕጎቼንና ሥርዐቶቼን ሁሉ ይጠብቁ፤ ሰንበታቴንም ቅዱስ አድርገው ይጠብቁ::

[25]“ካህን ወደ ሞተ ሰው ሬሳ በመጠጋት ራሱን አያርክስ፤ ይሁን እንጂ ሟች አባቱ ወይም እናቱ፣ ወንድ ልጁ ወይም ሴት ልጁ፣ ወንድሙ ወይም ያላገባች እኅቱ ብትሆን፣ ራሱን ማርከስ ይችላል:: [26]ከነጻም በኋላ፣ ሰባት ቀን መቈየት አለበት:: [27]በመቅደሱ ለማገልገል፣ ወደ መቅደሱ ውስጠኛው አደባባይ በሚገባበት ቀን፣ ስለ ራሱ የኀጢአት መሥዋዕት ያቅርብ፤ ይላል *ጌታ እግዚአብሔር*::

[28]“ለካህናቱ ርስታቸው እኔ ብቻ ነኝ፤ በእስራኤል ምንም ዐይነት ርስት አትስጧቸው፤ እኔ ርስታቸው እሆናለሁ:: [29]የእህሉን ቍርባን፣ የኀጢአቱንና የበደሉን መሥዋዕት ይበላሉ፤ በእስራኤል ለእግዚአብሔር የተሰጠው[c] ሁሉ የእነርሱ ይሆናል:: [30]ከፍሬ

44+12 2ነገ16+10-16፤መዝ106+26፤ ኤር14+10፤18+15
44+13 ዘኍ18+3፤ ሕዝ16+61፤ሆሴ5+1
44+14 1ሳሙ2+36፤ 2ነገ23+9፤1ዜና23+28-32
44+15 ዘፀ29+13፤ 2ሳሙ8+17፤ዕዝ7+2፤ ኤር33+18፤ሕዝ 40+46፤ዘካ3+7
44+16 ዘሌ3+16-17፤17+5-6፤ ዘኍ18+5፤ 1ሳሙ2+35፤ ሕዝ41+22፤ዘካ3+7
44+17 ራእ19+8
44+18 ዘፀ28+39፡42፤ዘሌ16+4፤ ኢሳ3+20
44+19 ዘፀ39+27-29፤ዘሌ6+10-11፡27፤ ሕዝ42+14
44+20 ዘሌ21+5፤ ዘኍ6+5፤ሕዝ5+1
44+21 ዘሌ10+9
44+22 ዘሌ21+7
44+23 ዘፍ7+2፤ ዘሌ13+50፤15+31፤ ኤር15+19፤ሕዝ 22+26፤ሐጌ2+11-13
44+24 ዘሌ23+2፤ ዘዳ17+8-9፤19+17፤ 21+5፤1ዜና23+4፤ 2ዜና19+8
44+25 ዘሌ21+1-4
44+26 ዘኍ19+14
44+27 ዘሌ4+28፤ ዘኍ3+28፤6+11
44+28 ዘኍ18+20፤ ዘዳ18+1-2፤ ኢያ13+33
44+29 ዘሌ6+16፤ 27+21፤ዘኍ18+9፡14፤ ኢያ13+14
44+30 ዘሌ25+21፤ ዘኍ15+18-21፤ 18+12-13፤

[c]29 የዕብራይስጡ ቃል ዕቃዎችን ወይም ሰዎችን ለእግዚአብሔር ከመስጠት አኳያ የማይለወጥ መደበኛ መስጠትን ያመለክታል

ማለት ነው::

44+15 *ሳዶቅ፤* የሌዋዊነት የዘር ሐረግ ውስጥ የገባው ከአሮን ልጅ ከአልዓዛር የተወለደ በመሆኑ ነው (1ዜና6+50-53):: እርሱም በዳዊት ዘመን ከአብያታር ጋር ካህን በመሆን አገልግሎአል (8+17 እና ማብ ይመ፤ 15+24-29፤ 20+25 ይመ):: አብያታር የአዶንያስ ደጋፊ በሆነ ጊዜ፣ ሳዶቅ የሰሎሞን ደጋፊ ሆኖ በመገኘቱ የኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ የማገልገል ልዩ መብት ለእርሱና ለልጆቹ አግኝቶአል (1ነገ1 ይመ):: በኋላ ግን የሳዶቅ ልጆች ከአገልግሎታቸው ተወግደዋል፤ ነገር ግን የቍምራን (የሙት ባሕር ጥቅልል መጻሕፍት የተገኙበት) ማኅበረ ሰብ ለእነርሱ በታማኝነት ጸንተው ተገኝተዋል:: *በታማኝነት ያከናወኑት፤* ሕዝቅኤል ከዚህ በፊት በተናገረው የፍርድ ንግር ውስጥ ያልተነገረ ሐሳብ ነው (7+26፤ 22+26 እና የም8 መሪ ሐሳብ ይመ):: ከምዕ 40-48 በተገለጸው ዝርዝር ሐሳብ ውስጥ የሳዶቅ ልጆች ስለ ታማኝነታቸው ልዩ ትኵረት ተሰጥቶአቸዋል::

44+16 *እነርሱ ብቻ ... ይገባሉ፤* ሌዋውያን ዝቅ የተደረጉበትና ሳዶቃውያን ከፍ ከፍ ያሉበት ይህ ክፍል በሥርዐቱ መሠረት መንጻት ልዩ ትኵረት እንደተሰጠው ሲሆን፣ ይህም ከም40-48 ባለው ክፍል ውስጥ የሚገኝ ዐቢይ ሐሳብ ነው:: ስለዚህም ብቁ የሆኑት ብቻ በአገልግሎት ውስጥ ይሳተፋሉ:: *ገበታዬ፤* ይህ ገበታ ኀብስቱ የተቀመጠበት (41+22 እና ማብ ይመ) ወይም የእግዚአብሔር ምግብ የሚቀርብበት ትልቁ መሠዊያ ነው (ቍ7)::

44+17 *የበፍታ ፈትል፤* ከሱፍ ይልቅ የሚቀዘቅዝ ልብስ ነው (ቍ18 ይመ)::

44+18 *ጥምጥም፤* ሕዝቅኤልም እንዲሁ በራሱ ላይ ጠምጥሞአል (24+17)::

44+19 *ልብስ አውልቀው፤* በሥርዐቱ መሠረት እንዳይረክሱ ነው::

44+20 *የራሳቸውን ጠጕር አይላጩት፤* የሐዘን ሥርዐት ስለሆነ (7+18)፤ ሐዘንተኛው ከተላጨ የረከሰ ያደርገዋል (ዘሌ 21+1-5 ይመ):: *የራሳቸውን ጠጕር አያርዝሙት፤* ይህ ቢሆን ስእለትን እንደ መፈጸም ስለሚቈጠር፣ ካህኑን ከአገልግሎት ያስቀረዋል (ዘኍ 6+5፤ ሐሥ 21+23-26 ይመ)::

44+23 *በተቀደሰውና ባልተቀደሰው መካከል ያለውን ልዩነት፤* ሕዝቅኤል ትኵረት ካደረገባቸው ነገሮች አንዱ ይህ ነው:: በረከሰና ባልረከሰ ምግብ መካከል እንዲሁም ለመሥዋዕት የሚቀርበው እንስሳ እንከን ያለበት ወይም የሌለበት መሆኑን መግለጽና የእግዚአብሔርን ፈቃድ ማሳወቅ አስፈላጊነቱ ዋጋን ለመክፈል ነበር (ሚክ3+1)፤ ወይም ይህ ጕዳዩ ትኵረት አልተሰጠው ይሆናል (ኤር2+8፤ ሕዝ22+26 ይመ):: በጥሩ ምሳሌነቱ ሐጌ2+10-13 ይመ::

44+24 *ካህናት ዳኞች ሆነው ያገልግሉ፤* ይህ ከጥንት ጀምሮ የነበረ ከአገልግሎት ተግባራቸው አንዱ ነበር፤ (የ1ሳሙ 4+18 አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ በተጨማሪም 2ዜና19+8-11 ይመ)::

44+25 *ወደ ሞተ ሰው፤* በሥርዐቱ መሠረት በድን የነካ ሰው የረከሰ ይሆናል (ዘሌ21+1-3፤ ሐጌ2+13)::

44+28 *ምንም ዐይነት ርስት አትስጧቸው፤* ካህናት ምንም ዐይነት መሬት ሊኖራቸው አይገባም የሚለው ዐረፍተ ነገር ከዘኍ18+20፡23-24፤ ዘዳ10+9፤ ኢያ13+14፡33፤ 18+7 ጋር ይጣጣማል::

በኩራት ምርጥ የሆነው ሁሉ እንዲሁም ከልዩ ስጦታዎቻችሁ የመጀመሪያው ሁሉ ለካህናት ይሆናል፤ ለቤተ ሰዎቻችሁ ሁሉ በረከት እንዲሆን ከምድር የምታገኙትን መብል በኩራት ለእነርሱ ስጧቸው። [31]ካህናት ሞቶ የተገኘውን ወይም በዱር አራዊት የተዘነጠለውን ወፍም ይሁን ሌላ እንስሳ፣ ማንኛውንም ነገር መብላት የለባቸውም።

### የምድሪቱ አከፋፈል

**45** [1] "ምድሪቱን ርስት አድርጋችሁ በዕጣ በምትከፋፈሉበት ጊዜ፣ ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ[ሀ] ክንድ፣ ወርዱ ሃያ ሺህ ክንድ የሆነውን አንዱን ክፍል፣ *ለእግዚአብሔር* የተቀደሰ ስፍራ አድርጋችሁ ስጡ፤ ስፍራውም በሙሉ ቅዱስ ይሆናል፤ [2]ከዚሁም አምስት መቶ ክንድ በአምስት መቶ ክንድ፣ ዙሪያው አምሳ ክንድ ባዶ ቦታ ቀርቶ፣ ለመቅደሱ ይሁን። [3]ከተቀደሰውም ስፍራ ላይ ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ፣ ወርዱ ዐሥር ሺህ ክንድ ለካ፤ በዚህም ውስጥ መቅደሱ፣ ይኸውም ቅድስተ ቅዱሳኑ ይሆናል። [4]ይህም በቤተ መቅደሱ ውስጥ ለሚያገለግሉና፣ *በእግዚአብሔር* ፊት ለአገልግሎት ለሚቀርቡ ካህናት፣ ቅዱስ የሆነ የምድሪቱ ክፍል ይሆናል። [5]ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ፣ ወርዱም ዐሥር ሺህ ክንድ ስፋት ያለው ስፍራ መኖሪያ ከተሞቻቸውን እንዲከትሙ[ለ] በቤተ መቅደስ ለሚያገለግሉ ሌዋውያን ርስት ይሆናል።

[6] "ከተቀደሰው ስፍራ ጋር የተያያዘ ወርዱ አምስት ሺህ ክንድ፣ ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ የሆነ ቦታ ለከተማዪቱ ርስት አድርገህ ስጥ፤ ይህም ለመላው የእስራኤል ቤት ይሆናል።

[7] "ገዢ ከቅዱሱ ስፍራና ከከተማው ወሰን ግራና ቀኝ ርስት ይኖረዋል፤ ይህም ከምዕራብ በኩል ወደ ምዕራብ አቅጣጫ ምሥራቅ በመዝለቅ፣ ከምዕራብ እስከ ምሥራቅ ያለውን ወሰን ርዝመት ተከትሎ ለአንዱ ነገድ ከተሰጠው ርስት ጋር ጐን ለጐን ይሄዳል። [8]ይህም መሬት በእስራኤል ምድር የገዢ ርስት ይሆናል። ከእንግዲህ ገዦቼ ሕዝቤን አይጨቍኑም፤ ነገር ግን የእስራኤል ቤት በየነገዳቸው ርስት እንዲይዙ ይፈቅዱላቸዋል።

[9] "ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'የእስራኤል ገዦች ሆይ! ከልክ ዐልፋችኋል፤ ይብቃችሁ፤ ዐመፅንና ጭቈናን ተዉ፤ ቀናና ትክክል የሆነውን ነገር አድርጉ። የሕዝቤን ርስት መቀማት ይቅርባችሁ፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*። [10]ትክክለኛ ሚዛን ትክክለኛ ኢፍና[+] ትክክለኛ ባዶስ[ሐ] ይኑራችሁ። [11]የኢፍና የባዶሱ መመዘኛ ተመሳሳይ ይሁን፤ አንድ ባዶስ የሆመር[+] አንድ ዐሥረኛ እንዲሁም አንድ ኢፍ የሆመር አንድ ዐሥረኛ ይሆናል፤ ሆመር ለሁለቱም ሚዛኖች መደበኛ መለኪያ ነው። [12]አንድ ሰቅል ሃያ ጌራህ የሚይዝ ይሆናል፤ በሃያ ሰቅል ላይ ሃያ አምስት ሰቅልና ዐሥራ አምስት ሰቅል ሲጨመር አንድ ምናን ይሆናል።'

### ልዩ ልዩ መሥዋዕትና በዓላት

[13] "የምታቀርቡት ልዩ መባ ይህ ነው፤ 'ከአንድ ሆመር መስፈሪያ ስንዴ አንድ ስድስተኛ ኢፍ እንዲሁም ከእያንዳንዱ ሆመር ገብስ አንድ ስድስተኛ ኢፍ ነው። [14]ዘይቱ

2ዜና31፥5፤ 10፤ነህ10፥35-37
44፥31 ዘፀ22፥31፤ ዘሌ11፥39፡40
45፥1 ዘኍ34፥13፤ ሕዝ48፥8-9፡29
45፥2 ሕዝ42፥20
45፥4 ሕዝ40፥46፤ 48፥10-11
45፥5 ሕዝ48፥13
45፥6 ሕዝ48፥15-18
45፥7 ሕዝ48፥21
45፥8 ዘኍ26፥53፤ ሕዝ46፥18
45፥9 መዝ12፥5፤ ኤር22፥3፤ዘካ7፥9-10፤8፥16
45፥10 ዘሌ19፥36፤ ዘዳ25፥15፤ምሳ11፥1፤ አሞ8፥4-6፤ሚክ6፥10-11
45፥11 ኢሳ5፥10
45፥12 ዘፀ30፥13፤ ዘሌ27፥25፤ዘኍ3፥47
45፥15 ዘሌ1፥4፤ 6፥30

[ሀ]1 ሰብዓ ሊቃናትም (በተጨማሪ ቍ3፣ 5እና 48፥9 ይመ) እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *ዐሥር ሺህ* ይላል
[ለ]5 ሰብዓ ሊቃናትም እንዲሁ ሲሆን ዕብራይስጡ ግን *በቤተ መቅደስ ... ሃያ ክፍሎች በንብረትነት ይኖራቸዋል*
[+]10 ኢፍ የደረቅ ነገር መስፈሪያ ነው
[ሐ]10 ባዶስ የፈሳሽ ነገር መለኪያ ነው
[+]11 ሆመር የደረቅ ነገር መስፈሪያ ነው

44፥31 *ሞቶ የተገኘውን፤* ይህ ገደብ በዘሌ7፥24 መሠረት እስራኤላውያንን በሙሉ የሚመለከት ነው።

45፥1 *ምድሪቱን ... በዕጣ በምትከፋፈሉበት ጊዜ፤* የመሬት ይዞታን እንደ ገና መከፋፈልን ያመለክታል። *ለእግዚአብሔር ... ስጡ፤* በምድሪቱ መካከል ያለው ባለአራት ማእዘን ስፍራ በሙሉ፣ ለእግዚአብሔር የተለየ ይሆናል። *ሃያ ሺህ ክንድ፤* አንድ ጐኑ ባለ አምስት ሺህ ክንድ የሆነው ይህ ከተማ (ቍ6)፣ ርዝመቱና ወርዱ ፍጹም እኩል የሆነ ባለ አራት ማእዘን ነው። *ስፍራውም በሙሉ ቅዱስ ይሆናል፤* በማንኛውም ነገድ ያልተያዘና ለእግዚአብሔር የተለየ ማለት ነው።

45፥2 *አምስት መቶ ክንድ በአምስት መቶ ክንድ፤* በ42፥16-20 ላይ የተገለጸው ለቤተ መቅደሱ የሚሆን ስፍራ ነው። *ባዶ ቦታ፤* ስፍራው በሙሉ የተቀደሰ ቢሆንም (42፥20 ይመ)፣ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ግን፣ ቅዱስ በሆነውና እጅግ ቅዱስ በሆነው መካከል ያልተያዘውን ቦታ ነው።

45፥3 *ስፍራ ... ለካ፤* በመካከል ያለው ባለ አራት ማእዘኑ የተቀደሰ ስፍራ፣ በተለይ ለቤተ መቅደሱ የሚሆን ነው።

45፥4 *ለሚያገለግሉ ... ካህናት፣ ቅዱስ የሆነ የምድሪቱ ክፍል ይሆናል፤* በርስትነት የሚይዙት ሳይሆን (44፥28 ይመ)፤ እንዲኖሩበት ብቻ ነው።

45፥5 *ስፍራ ... ለሚያገለግሉ ሌዋውያን፤* ቦታው የተቀደሰ ቢሆንም፣ ለሌዋውያኑ መኖሪያ እንዲሆን በስተ ሰሜን በኩል እኩል ስፋት ያለው ስፍራ ተሰጥቶአል። ለካህናቱ ለሳዶቅ ልጆች እንደተደነገገባቸው ሳይሆን፣ ሌዋውያን መሬት በርስትነት መያዝ ይችሉ ነበር።

45፥6 *ለከተማዪቱ፤* የቀድሞዋ ኢየሩሳሌም ይዞታ፣ የቤተ መቅደሱንም ክልል በውስጡ የሚያካትት ነበር። የአዲሲቱ ቅድስት ከተማ ይዞታ ግን እንደ ቀድሞው፣ ከቤተ መቅደሱ ቀጥሎ የሚገኝ ስፍራ ነው። *ወርዱ አምስት ሺህ ክንድ፤* የከተማዪቱ ደቡባዊ ክልል፣ ከተማዪቱን በትክክል በለአራት ማእዘን ያደርጋታል። *ለመላው የእስራኤል ቤት ይሆናል፤* እንደ ቀደሙት ዘመናት ለየትኛውም ነገድ ወይም ሰው አይሆንም ማለት ነው።

45፥7 *ገዢው ... ርስት ይኖረዋል፤* ከግዛቱ የተወሰነው ክፍል ለእርሱ ይሆናል ማለት ነው። በቍ8 መሠረት (ከ46፥18 ጋር ያነጻጽሩ)፣ እንደ አክዓብ (1ነገ21) ስግብግብ እንዳይሆን፣ ይህ መሬት ለገዢው የሚሰጥ ይሆናል። ገዢውም በበኩሉ በየበዓላቱ አስፈላጊ መሥዋዕቶችን የማቅረብ ግዴታ ይጠበቅበታል (ቍ17)።

45፥9 *የእስራኤል ገዦች ሆይ፤* በዚህ ቍጥር ላይ ያለው አገላለጽ፣ ሕዝቅኤል ከ586 ዓ.ቅ.ክ. በፊት ይሰብክ ለነበረው ዐቢይ ሐሳብ ቀሪ ነው (22፥6 ይመ)።

45፥10 *ትክክለኛ ሚዛን ... ይኑራችሁ፤* ቀድሞ የነበረውን ኢፍትሐዊ የኢኮኖሚ ሥርዐት እስራኤል ደግማ ልትከተል አይገባትም። የብሉይ ኪዳን በሚዛንና በመለኪያ የሚደረግን ማታለል ያወግዛል (ዘሌ19፥35-36፤ ዘዳ25፥13-16፤ ሚክ6፥10-12 ይመ)።

45፥11 *ተመሳሳይ ይሁን፤* ከዐሥራ ስምንት ሊትር በላይ ትንሽ ከፍ ይበል ማለት ነው። *ሆመር፤* ሁለት መቶ ሃያ ሊትር ነው።

45፥13 *ልዩ መባ፤* ለካህናቱ የሚሰጥ ሳይሆን፣ (44፥30) ለገዢው የሚሰጠው ነው። ገዢውም ከእነዚህ መባዎች ከፊሉን ለእግዚአብሔር ይሰጣል (ቍ16 ይመ)።

በባዶስ ሲለካ የተወሰነው መስፈሪያ ከእያንዳንዱ ሆመር አንድ ዐሥረኛ ባዶስ ይሆናል፤ ይኸውም ዐሥር ባዶስ ወይም አንድ ሆመር ነው፤ ዐሥር ባዶስ ከአንድ ሆመር ጋር እኩል ነውና። [15]እንዲሁም ውሃ ከጠገበው ከእስራኤል መሰማሪያ፣ ሁለት መቶ በግ ካለው ከእያንዳንዱ መንጋ አንድ በግ ይውሰድ። ይህ ሁሉ ለሕዝቡ ማስተስረያ ለሚሆነው ለእህል ቍርባን፣ ለሚቃጠል መሥዋዕትና ለኅብረት መሥዋዕት* ይውላል፤ ይላል ጌታ *እግዚአብሔር*። [16]የምድሪቱ ሕዝብ ሁሉ ይህን ልዩ መባ ለእስራኤል ገዥ ይሰጣሉ። [17]በበዓላት፣ በወር መባቻና በሰንበታት፣ ለእስራኤል ቤት በተወሰኑት በዓላት ሁሉ የሚቃጠል መሥዋዕት፣ የእህል ቍርባንና የመጠጥ ቍርባን ማቅረብ የገዡ ኀላፊነት ነው፤ ለእስራኤል ቤት ማስተስረያ እንዲሆንም የኀጢአት መሥዋዕት፣ የእህል ቍርባን፣ የሚቃጠል መሥዋዕትና የኅብረት መሥዋዕት ያቀርባል።’

[18]“ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ‘በመጀመሪያው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን ነውር የሌለበትን ወይፈን ውሰድ፤ መቅደሱንም አንጻው። [19]ካህኑም ከኀጢአቱ መሥዋዕት ደም በመውሰድ በቤተ መቅደሱ በር መቃኖች፣ በመሠዊያው ላይኛ ዕርከን አራት ማእዘንና በውስጠኛው አደባባይ በር መቃኖች ላይ ይርጨው። [20]አንድ ሰው ሳያስብ ወይም ባለማወቅ ኀጢአት ቢሠራ፤ ወር በገባ በሰባተኛው ቀን ይህን ታደርጋለህ፤ በዚህ ዐይነት ለቤተ መቅደሱ ታስተሰርያላችሁ።’

[21]“ ‘በመጀመሪያው ወር በዐሥራ አራተኛው ቀን የፋሲካን በዓል ታከብራላችሁ፤ ይህም እርሾ የሌለበትን እንጀራ የምትበሉበት ሰባት ቀን የሚከበር በዓል ነው። [22]በዚያም ቀን ገዢው ስለ ራሱና ስለ ምድሪቱ ሕዝብ ሁሉ አንድ ወይፈን የኀጢአት መሥዋዕት አድርጎ ያቀርባል። [23]በዓሉ በሚከበርበት በሰባቱ ቀን ገዡ በየዕለቱ እንከን የሌለባቸውን ሰባት ወይፈኖችና ሰባት አውራ በጎች የሚቃጠል መሥዋዕት አድርጎ ለ*እግዚአብሔር* ያቅርብ፤ በየዕለቱም ለኀጢአት መሥዋዕት አውራ ፍየል ያቅርብ። [24]ለአንዱ ወይፈን አንድ የኢፍ መስፈሪያ፣ ለአንድ አውራ በግ አንድ የኢፍ መስፈሪያ የእህል ቍርባን አድርጎ፣ ለእያንዳንዱም ኢፍ አንድ የኢን መስፈሪያ ዘይት አብሮ ያቅርብ።

[25]“ ‘በሰባተኛው ወር በዐሥራ አምስተኛው ቀን በሚጀመረው በሰባቱ ቀን በዓል፣ ለኀጢአት መሥዋዕት፣ ለሚቃጠል መሥዋዕት፣ ለእህል ቍርባንና ለዘይቱም እንዲሁ ያቅርብ።

45፥17 ዘሌ23፥38፤ ዘኍ10፥10፤15፥8-62፤2ዜና31፥3፤ኢሳ 66፥23፤ሕዝ46፥4-12
45፥18 ዘፀ12፥2፤ ዘሌ 16፥33፤22፥20፤ ዕብ9፥14
45፥19 ዘሌ16፥18 -19፤ሕዝ43፥17
45፥20 ዘሌ4፥27
45፥21 ዘፀ12፥11
45፥22 ዘሌ4፥14
45፥23 ዘኍ22፥40፤ 28፥16-25፤ኢዮ42፥8
45፥24 ዘኍ28፥12 -13፤ሕዝ46፥5-7
45፥25 ዘሌ23፥34 -43፤ዘኍ29፥12-38፤ ዘዳ16፥13
46፥1 ቍ6፤1ዜና 9፥18፤ኢሳ66፥23፤ ሕዝ40፥19
46፥2 ቍ8፡12፤ ሕዝ40፥39፤44፥3
46፥3 ኢሳ66፥23፤ ሉቃ1፥10
46፥5 ቍ11
46፥6 ቍ1፤ዘሌ 22፥20፤ዘኍ10፥10
46፥7 ሕዝ45፥24

**46** “ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ለምሥራቅ ትይዩ የሆነው የውስጠኛው አደባባይ በር በስድስቱ የሥራ ቀኖች ይዘጋ፤ ነገር ግን በሰንበት ቀንና በወር መባቻ ቀን ይከፈት። [2]ገዢ ከውጭ በኩል በመግቢያው መተላለፊያ በረንዳ በመግባት በበሩ መቃን አጠገብ ይቁም፤ ካህናቱም የእርሱን የሚቃጠል መሥዋዕትና የኅብረት መሥዋዕት[1] ያቅርቡለት፤ በበሩ መግቢያ ደፍ ላይ ሆኖ ይስገድ፤ ከዚያም ይውጣ፤ በሩ ግን እስከ ምሽት ድረስ አይዘጋ። [3]የምድሪቱም ሕዝብ በሰንበታትና በወር መባቻ በዓላት በ*እግዚአብሔር* ፊት በበሩ መግቢያ ላይ ይስገዱ። [4]ገዢ በሰንበት ቀን በ*እግዚአብሔር* ፊት የሚያቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት ስድስት የበግ ጠቦትና አንድ አውራ በግ ነው፤ ሁሉም እንከን የሌላቸው ይሁኑ። [5]ከአውራ በጉ ጋር የሚቀርበው የእህል ቍርባን አንድ የኢፍ መስፈሪያ ይሁን፤ ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የሚቀርበውም የእህል ቍርባን ሰውየው የወደደውን ያህል ይሁን፤ እያንዳንዱም የኢፍ መስፈሪያ አንድ የኢን መስፈሪያ ዘይት ይኑረው። [6]በወር መባቻ በዓል አንድ ወይፈን፣ ስድስት የበግ ጠቦትና አንድ አውራ በግ ያቅርብ፤ ሁሉም እንከን የሌለባቸው ይሁኑ። [7]ከወይፈኑ ጋር አንድ የኢፍ መስፈሪያ፣ ከአውራው በግም ጋር አንድ የኢፍ መስፈሪያ የእህል ቍርባን ያቅርብ፤ ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የሚቀርበው የእህል ቍርባን ደግሞ ሰውየው የወደደውን ያህል ይሁን፤ እያንዳንዱም የኢፍ መስፈሪያ

*15 በትውፊት *የድነት መሥዋዕት* ይባላል
[1]2 በትውፊት *የድነት መሥዋዕት* ይባላል፤ እንዲሁም በቍ 17

45፥17 ***የመጠጥ ቍርባን፤*** ሊሰጥ የሚገባው የወይን ጠጅ ሆኖ ሳለ (ዘኍ15፥5፤ ሆሴ9፥4 ይመ)። እዚህ ላይ ዘይት እንጂ (ቍ 14:24) የወይን ጠጅ አልተጠቀሰም።

***45፥18-46፥24፤*** በዚህ ክፍል የተገለጸው ሐሳብ በሙሴ ሕግ ከሚገኘው ጋር ብዙ ልዩነት አለው፤ የአይሁድ መምህራንም እስካሁን ልዩነቶች ለማስታረቅ ሞክረዋል። ለምሳሌ፦ በ45፥18 ላይ የተጠቀሰው በየዓመቱ የሚደረገው የቤተ መቅደስ ማንጻት ሥርዓት፣ በዘሌዋውያን 16 ላይ ከተጠቀሰው ከስርየት ቀን ሥርዐት ጋር ምንም ዐይነት ግንኙነት የለውም ይላሉ።

45፥19 ***ካህኑም፤*** ሊቀ ካህኑን ማለት ነው።

45፥22 ***የኀጢአት መሥዋዕት፤*** የ40፥39 ማብ ይመ።

45፥25 ***በሰባተኛው ወር ... በሚጀመረው ... በዓል፤*** ከብዙ ሁኔታዎች አኳያ፣ እጅግ በጣም አስፈላጊ የሚባሉት በዓላት፣ የመከር በዓልና (ዘፀ23፥16፤ 34፥22) የዳስ በዓል ናቸው (ዘዳ 16፥16)።

46፥1 ***የውስጠኛው አደባባይ በር፤*** የውጪው አደባባይ የምሥራቅ በር ምንጊዜም ዝግ ሲሆን (44፥2)፣ የውስጠኛው አደባባይ የምሥራቁ በር ግን፣ በበዓላት ቀን ሊከፈት ይችላል።

46፥2 ***በመግቢያው መተላለፊያ በረንዳ፤*** የውስጠኛው አደባባይ በር መተላለፊያ በረንዳ፣ ከውጪው አደባባይ ጋር ትይዩ ነው። ***በበሩ መቃን አጠገብ ይቁም፤*** ይህ በር በሥርዐቱ መሠረት የነጻ ነው (45፥19)። ገዥው እዚህ ቦታ ቆሞ በውስጠኛው አደባባይ በትልቁ መሠዊያ ላይ የሚቀርቡትን መሥዋዕቶች መስፍኑ ሊመለከት ይችላል፤ ነገር ግን ወደ ውስጠኛው አደባባይ መግባት አይፈቀድለትም።

46፥3 ***በበሩ መግቢያ፤*** ይኸኛው መግቢያ በውጪው አደባባይ የሚገኝ ነው።

46፥4 ***ስድስት የበግ ጠቦትና አንድ አውራ በግ፤*** በሙሴ ሕግ ከተጻፈው ጋር ሲነጻጸር ልዩነት ለመኖሩ፣ ይኸኛው ሌላ ማስረጃ ነው (በ45፥18-46፥24 ያለውን ማብ ይመ)። በዘኍ 28፥9 የታዘዘው ሁለት ጠቦት ብቻ ሲሆን፣ በሰንበት ግን አውራ አይቀርብም።

46፥5 ***ኢፍ፤*** ከዘኍ28፥9 ጋር ያወዳድሩ።

46፥6 ***በወር መባቻ፤*** የወሩ የመጀመሪያ ቀን ነው። ይህን በዘኍ 28፥11 ከተጠቀሰው አስፈላጊ ነገር ጋር ያነጻጽሩ።

46፥7 ***አንድ የኢፍ መስፈሪያ የእህል ቍርባን፤*** ከዘኍ 28፥12 ጋር ያነጻጽሩ።

የኢን መስፈሪያ ዘይት ይኑረው። [8]ገዢ ሲገባ፣ በመግቢያው በር መተላለፊያ በረንዳ ይግባ፤ ሲወጣም በዚያው ይውጣ።

[9]“ ‘በተወሰኑት በዓላት የምድሪቱ ሕዝብ *በእግዚአብሔር* ፊት በሚቀርብበት ጊዜ፣ ይሰግድ ዘንድ በሰሜን በር የገባ ሁሉ በደቡብ በር ይውጣ፤ በደቡብ በር የገባም በሰሜኑ በር ይውጣ፤ በፊት ለፊቱ ባለው በር ይመለስ እንጂ ማንም በገባበት በር አይውጣ። [10]ገዢ በመካከላቸው በመሆን፣ ሲገቡ ይገባል፤ ሲወጡም ይወጣል።

[11]“ ‘በበዓላትና በተወሰኑት በዓላት፣ ከወይፈኑ ጋር አንድ የኢፍ መስፈሪያ፣ ከአውራ በጉም ጋር አንድ የኢፍ መስፈሪያ የእህል ቍርባን ያቅርብ፤ ከበግ ጠቦቶቹ ጋር የሚያቀርበው የእህል ቍርባን ግን ሰውየው የወደደውን ያህል ይሁን፤ እያንዳንዱም የኢፍ መስፈሪያ አንድ የኢን መስፈሪያ ዘይት ይኑረው። [12]ገዢ በፈቃዱ *ለእግዚአብሔር* የሚቃጠል መሥዋዕትም ሆነ የኅብረት መሥዋዕት በሚያቀርብበት ጊዜ፣ በምሥራቅ ትይዩ የሆነው በር ይከፈትለት፤ በሰንበት ቀን እንደሚያደርገው ሁሉ የሚቃጠል መሥዋዕቱንም ሆነ የኅብረት መሥዋዕቱን ያቅርብ፤ ከዚያ በኋላ ይወጣል፤ በሩም ይዘጋል።

[13]“ ‘በየቀኑ እንከን የሌለበትን የአንድ ዓመት ጠቦት የሚቃጠል መሥዋዕት አድርገህ *ለእግዚአብሔር* አቅርብ፤ ይህንንም በየማለዳው ታቀርበዋለህ። [14]ከዚህም ጋር አንድ ስድስተኛ የኢፍ መስፈሪያ ዱቄት መለወሻም የሚሆን የኢን መስፈሪያ ሢሶ ዘይት አድርገህ በየማለዳው የእህል ቍርባን አቅርብ፤ ይህን የእህል ቍርባን *ለእግዚአብሔር* ማቅረብም የዘላለም ሥርዐት ነው። [15]ስለዚህ ዘወትር ለሚቀርበው የሚቃጠል መሥዋዕት በየማለዳው የበግ ጠቦት፣ የእህል ቍርባንና ዘይት ይቅረብ።

[16]“ ‘ጌታ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ ገዢ ከርስቱ ላይ ከወንድ ልጆቹ ለአንዱ ስጦታ ቢያደርግ፣ ያ ስጦታ ለዘሩ የሚተላለፍ ነው፤ በውርስም ንብረታቸው ይሆናል። [17]ይሁን እንጂ ገዢ ከርስቱ ላይ ከባሪያዎቹ ለአንዱ ቢሰጥ፣ ባሪያው ነጻ እስከሚወጣበት ዓመት ድረስ የራሱ ሊያደርገው ይችላል፤ ከዚያም ርስቱ ለገዢ ይመለስለታል፤ ርስቱም ለወንድ ልጆቹ ብቻ የሚተላለፍ ይሆናል፤ የእነርሱም ነው። [18]ገዢ ከንብረታቸው በማፈናቀል፣ የትኛውንም የሕዝቡን ርስት መውሰድ አይገባውም፤ ለወንድ ልጆቹ ርስት መስጠት ያለበት ከራሱ ንብረት ነው፤ ይኸውም ከሕዝቤ ማንም ከርስቱ እንዳይነቀል ነው።’ ”

[19]ከዚያም ያ ሰው በበሩ አጠገብ ባለው መግቢያ አድርጎ፣ ለሰሜን ትይዩ ወደ ሆኑት ወደ ካህናቱ የተቀደሱ ክፍሎች አመጣኝ፤ በምዕራቡም መዳረሻ ያለውን ቦታ አሳየኝ። [20]እርሱም፣ “ይህ ስፍራ ሕዝቡን ለመቀደስ መሥዋዕቱን ወደ ውጩ አደባባይ እንዳያወጡ፣ ካህናቱ የበደሉን መሥዋዕትና የኀጢአቱን መሥዋዕት የሚቀቅሉበት፣ የእህሉንም ቍርባን የሚጋግሩበት ቦታ ነው” አለኝ።

[21]ከዚያም ወደ ውጩ አደባባይ አመጣኝ፤ በአራቱም ማእዘን ዙሪያ መራኝ፤ በእያንዳንዱም ማእዘን ሌላ አደባባይ አየሁ። [22]በውጩ አደባባይ ባለው በአራቱ ማእዘን የታጠሩ[1] አደባባዮች አሉ፤ ርዝመታቸው አርባ ክንድ፣ ወርዳቸውም ሠላሳ ክንድ ነበር፤ በአራቱም ማእዘን ያሉት አደባባዮች እኩል ናቸው። [23]ከሥሩ ዙሪያውን ምድጃ የነበረበት፣ በአራቱም አደባባዮች ውስጥ ዙሪያ የድንጋይ ዕርከን ነበር። [24]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ “እነዚህ፣ በቤተ መቅደሱ የሚያገለግሉቱ፣ የሕዝቡን መሥዋዕት የሚቀቅሉባቸው ስፍራዎች ናቸው።”

## ከቤተ መቅደሱ ተነሥቶ የሚፈሰው ወንዝ

**47** ከዚያም ያ ሰው ወደ ቤተ መቅደሱ መግቢያ መልሶ አመጣኝ፤ ከቤተ መቅደሱ መድረክ ሥር ውሃ እየወጣ፣ ወደ ምሥራቅ ይፈስ ነበር፤ ቤተ መቅደሱ ለምሥራቅ ትይዩ ነበርና። ውሃው ከቤተ መቅደሱ በስተ ደቡብ በኩል፣ በመሠዊያው ደቡብ በኩል፣ ሥር ሥሩን ይወርዳል። [2]ከዚያም በሰሜኑ በር በማውጣት በውጭ አዞሮ በምሥ

46፥8 ቍ 2፤ ሕዝ44፥3
46፥9 ዘፀ23፥14፤ 34፥20
46፥10 2ሳሙ6፥14-15፤መዝ42፥4
46፥11 ቍ5
46፥12 ቍ 2፤ ዘሌ 7፥16፤ ሕዝ45፥17
46፥13 ዘፀ29፥38፤ ዘኍ28፥3፤መዝ5፥3
46፥14 ዘኍ15፥6፤ ዳን8፥11
46፥15 ዘፀ29፥38፤ 42፤ዘኍ28፥5-6
46፥16 2ዜና21፥3
46፥17 ዘሌ25፥10
46፥18 ዘሌ25፥23፤ 1ሳሙ8፥14፤ ሕዝ45፥8፤ሚክ2፥1-2
46፥19 ሕዝ42፥4፡9
46፥20 ቍ 24፤ ዘሌ 6፥27፤ዘካ14፥20
47፥1 መዝ46፥4፤ ኢሳ55፥1፤ኢል3፥18፤ ራእ22፥1
47፥2 ሕዝ40፥35

[1]22 በዕብራይስጥ የዚህ ቃል ትርጕም አይታወቅም

46፥9 *በሰሜን በር የገባ ሁሉ፤* ይህ የሕዝብን ብዛት ለመቈጣጠር ታስቦ የተደረገ ይመስላል። ይህ ካልሆነ ግን ወደ ፊት በሚመጣው ዘመን በበዓል ቀን ብዙ ሕዝብ ወደ መቅደሱ እየተጋፋ ይገባል ማለት ነው።

46፥12 *በፈቃዱ ... መሥዋዕትም ... በሚያቀርብበት ጊዜ፤* ገዥው በሕጉ መሠረት ማቅረብ ከሚገባው በላይ እንደ ፍላጐቱ የሚያቀርበው ነው።

46፥13 *በየማለዳው፤* በየቀኑ ጠዋት አንድ ጠቦትና በምሽት ላይ ሌላ አንድ ጠቦት እንዲሠዋ ከታዘዘበት ከዘኍ 28፥3-8 ጋር ይህን ያነጻጽሩ (1ዜና16፥40፤ 2ዜና13፥11፤ 31፥3 ይመ)። ጠዋት የሚቃጠል መሥዋዕት፣ በየምሽትም የእህል ቍርባን የሚቀርብበት ለየት ያለ ልማድ በ2ነገ16፥15 ላይ ተጠቅሶአል።

46፥14 *አንድ ስድስተኛ የኢፍ መስፈሪያ ... የኢን መስፈሪያ ሢሶ፤* ከዘኍ28፥5 ጋር ያወዳድሩ።

46፥16 *ለዘሩ፤* ሕዝቅኤል እዚህ ላይ የሚያሳየው ከትውልድ ወደ ትውልድ በውርስ የሚተላለፈውን አመራር ነው።

46፥17 *ነጻ እስከሚወጣበት ዓመት ድረስ፤* የኢዮቤልዩ ዓመት የሚባለው ነው፤ ይህም የሚከበረው በየአምሳ ዓመት አንድ ጊዜ ነው (ዘሌ25፥8-15 በተለይም ቍ13 ይመ)።

46፥18 *ገዥው ... መውሰድ አይገባውም፤* የ45፥7 ማብ ይመ።

*46፥19-24፤* ይህ ካህናት ሌሎች ክፍሎች እንዳሏቸው በዝርዝር ከተገለጸበት ከ42፥13-14 ጋር በእጅጉ ይመሳሰላል። በዚህ ስፍራ የተገለጹት ስጦታዎች መሥዋዕት ስለማቅረብ ከተሰጠው ሕግ ጋር የሚመሳሰሉ ናቸው። ለካህናት የተሰጠው ስፍራ (ቍ19-20)፣ ሌዋውያን ምግባቸውን ከሚያበስሉበት ክፍል የተለየ ነው (ቍ21-24)።

47፥1 *ያም ሰው፤* ለመጨረሻ ጊዜ እዚህ ላይ የተጠቀሰው፣ መሪው መልአክ (40፥3)፣ የሕዝቅኤልን አዲስ ቤተ መቅደስ የራእይ ጕዞ ያጠናቅቃል። *ወደ ቤተ መቅደሱ መግቢያ፤* ሕዝቅኤል የቆመው በውስጠኛው አደባባይ ነበር። *ውሃ፤* ከዚህ የሚቀጥለው ክፍል (ቍ1-12)፣ ውሃው ፈዋሽና ሕይወት ሰጭ መሆኑን በግልጽ ያመለክታል (መዝ36፥8፤ 46፥4 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢል3፥18፤ ዘካ13፥1፤ 14፥8፤ ራእ22፥1-2 ይመ)። የዚህ ሐሳብ መሠረቱ፣ ከኤደን ገነት ተነሥቶ የሚፈሰው ወንዝ ነው (ዘፍ2፥10)።

47፥2 *በሰሜኑ በር በማውጣት፤* ይህ የሆነበት ምክንያት፣

ራቅ አቅጣጫ ወዳለው የውጭ በር መራኝ፤ ውሃውም በደቡብ በኩል ይፈስ ነበር::

[3]ያም ሰው የመለኪያውን ገመድ በእጁ ይዞ ወደ ምሥራቅ በመሄድ፣ አንድ ሺህ ክንድ ለካ፤ ከዚያም እስከ ቁርጭምጭሚት በሚደርሰው ውሃ ውስጥ መራኝ፤ [4]ቀጥሎም አንድ ሺህ ክንድ ለካ፤ እስከ ጕልበት ወደ ሚደርስም ውሃ መራኝ፤ ከዚያም ሌላ አንድ ሺህ ክንድ ለካ፤ እስከ ወገብ ወደሚደርስም ውሃ መራኝ:: [5]እንደ ገናም አንድ ሺህ ክንድ ለካ፤ አሁን ግን ልሻገረው የማልችል ወንዝ ሆነ፤ ምክንያቱም ውሃው ስለ ሞላና ጥልቅ ስለ ነበረ፣ በዋና ካልሆነ በስተቀር በእግር ሊሻገሩት የማይቻል ነበር:: [6]እርሱም፣ "የሰው ልጅ ሆይ፤ ይህን ታየዋለህን?" ሲል ጠየቀኝ::

ከዚያም መልሶ ወደ ወንዙ ዳር መራኝ፤ [7]እዚያም በደረስሁ ጊዜ፣ በወንዙ ግራና ቀኝ ብዙ ዛፍ አየሁ:: [8]እርሱም እንዲህ አለኝ፤ "ይህ ውሃ ወደ ምሥራቅ ምድር ይፈሳል፤ ወደ ባሕሩ ወደሚገባበት ወደ ዓረባ[ነ] ይወር ዳል፤ ወደ ባሕሩም[ለ] ሲፈስ፣ በዚያ የነበረው ውሃ ንጹሕ ይሆናል:: [9]ወንዙ በሚፈስበት ስፍራ ሁሉ ብዙ ሕያዋን ፍጡራን ይኖራሉ:: ይህ ውሃ በዚያ ስለሚፈስና ጨውማ የሆነ ውን ውሃ ንጹሕ ስለሚያደርገው፣ ዓሣ በብዛት ይኖራል፤ ስለዚህ ወንዙ በሚፈስበት ስፍራ ሁሉ ማንኛውም ነገር በሕይወት ይኖራል:: [10]ዓሣ አጥማጆች በወንዙ ዳር ይቆማሉ፤ ከዓይ ንጋዲ እስከ ዓይንኤግላይም ድረስ ያለው ቦታ መረብ መዘርጊያ ይሆናል፤ ዓሣውም እንደ ታላቁ ባሕር[ሐ] ዓሣ፣ የተለያየ ዐይነት ይሆናል:: [11]ነገር ግን ረግረጉና ዕቋሪው ውሃ ንጹሕ አይሆንም፤ ጨው እንደ ሆነ ይቀራል:: [12]በወንዙም ዳርና ዳር፣ ፍሬ የሚያፈሩ የዛፍ ዐይነቶች ሁሉ ይበቅላሉ፤ ቅጠላቸው አይደ ርቅም፤ ፍሬ አልባም አይሆኑም:: ከመቅደሱ የሚወጣው ውሃ ስለሚፈስላቸው በየወሩ ያፈ ራሉ፤ ፍሬያቸው ለምግብ፣ ቅጠላቸውም ለፈውስ ይሆናል::

47+3 ሕዝ40+3
47+5 ዘፍ2+10፤ ኢሳ11+9፤ዕ32+14
47+7 ቍ2፤ ራእ 22+2
47+8 ዘዳ1+1፤ 3+17፤ኢሳ41+18
47+9 ኢሳ12+3፤ 55+1፤ዮሐ4+14፤ 7+37-38
47+10 ዘኍ34+6፤ ኢያ15+62፤ መዝ 104+25፤ ኢሳ19+8፤ ሕዝ26+5፤ማቴ4+19 ፤13+47
47+11 ዘጸ29+23
47+12 ቍ7፤ ዘፍ2+9፤መዝ1+3፤ ኢሳ55+1፤ኤር17+8፤ ሕዝ 36+8፤ ራእ22+2
47+13 ዘፍ48+16፤ 49+26፤ዘኍ34+2-12
47+14 ዘፍ12+7፤ ዘዳ1+8፤ሕዝ36+12
47+15 ቍ19፤ ዘኍ34+2፡6፤ ሕዝ48+1
47+16 ዘኍ13+21፤ 2ሳሙ8+8፤ ኤር49+23፤ ሕዝ48+1
47+17 ሕዝ48+1

## የምድሪቱ ወሰን

[13]ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ምድሪቱን ርስት አድርገህ ለዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል ነገድ የምታከፋፍሉባቸው፣ ወሰ ኖች እነዚህ ናቸው፤ ዮሴፍ ሁለት ዕጣ ይኑረው:: [14]እኩል አድርጋችሁ ከፋፍሉት፤ ለቀድሞ አባቶቻችሁ እሰጣቸው ዘንድ በተ ዘረጋች እጅ ስለ ማልሁ፣ ምድሪቱ ርስታችሁ ትሆናለች::

[15]"የምድሪቱ ወሰን ይህ ነው፤

"በሰሜን በኩል ከታላቁ ባሕር አንሥቶ በሔትሎን መንገድ በሐማት መተላለፊያ አድርጎ እስከ ጽዳድ ይደርሳል፤ [16]ከዚያም ቤሮታን፣[ዐ] በደማስቆና በሐማት ወሰን መካ ከል ያለውን ሲብራይምን ዐልፎ፣ በሐው ራን ወሰን ላይ እስካለው እስከ ሐጸርሃ ቲኮን ይዘልቃል:: [17]ወሰኑ ከባሕሩ በመነሣት፣

[ነ]8 ወይም *ወደ ዮርዳኖስ ሸለቆ*
[ለ]8 ሙት ባሕርን ያመለክታል
[ሐ]10 ሜድትራኒያንን ያመለክታል፤ እንዲሁም ቍ19 እና 20
[ዐ]15-16 ሰብዓ ሊቃናትንና ሕዝ48+1 ይመ፤ ዕብራይስጡ ግን ... *ወደ ጽዳድ የሚወስደው መንገድ፣ 16. ሐማት ቤሮታን* ... ይላል

---

የምሥራቅ በር ስለ ተዘጋ ነበር (44+2)::

47+5 *እንደገናም አንድ ሺህ ... ለካ፤* በአጠቃላይ የተለካው አራት ጊዜ ነው (የ1+5 ማብ ይመ):: *ሊሻገሩት የማይቻል፤* ገብር ወንዞች ሳይኖሩት፣ ሞልቶ መፍሰሱ የሚያስገርም ነው::

47+7 *ብዙ ዛፍ፤* የኤድን ገነት ቅሬታ ነው (ዘፍ2 9)::

47+8 *ወደ ምሥራቅ ምድር፤* ከዘካ14+8 ጋር ያወዳድሩ:: *ባሕሩ፤* አብዛኛውን ጊዜ የሚያመለክተው የሜዲትራኒያንን ባሕር ሲሆን፣ እዚህ ላይ ለማመልከት የታሰበው ግን ሙት ባሕርን ነው (አግራጭ ትርጕሙን ይመ):: *ዓረባ፤* በሙት ባሕርና በኢየሩ ሳሌም መካከል ያለ ውሃ አልባ የሆነ ስፍራ ነው (አግራጭ ትርጕሙን ይመ):: *ንጹሕ ይሆናል፤* በዕብራይስጥ ዘይቤያዊ አገላለጹ፣ "ይፈውሳል" ማለት ነው:: ከባሕር ወለል በታች 1300 ሜትር በሆነ ዝቅተኛ ስፍራ ሃያ አምስት በመቶ ጨዋማ በሆነው ውሃ ውስጥ፣ ይህን ያህል ብዙ ፍጥረት ማቆየቱ፣ "የሕይወት ውሃ ወንዝ" (ራእ 22+1) ያለውን አስደናቂ የመፈወስ ኀይል ያመለክታል::

47+9 *ብዙ ሕያዋን ፍጡራን፤* በዘፍ1+20-21 ላይ የሚገኘ ውን አዲስ ፍጥረትን ለማመልከት ተጠቅሞበታል::

47+10 *ዓይንጋዲ፤* "የፍየል ምንጭ ውሃ" ማለት ነው፤ ከሙት ባሕር በስተ ምዕራብ በኩል የሚገኝ ኀይለኛ የውሃ ምንጭ ነው፤ *ዓይንኤግላይም፤* "የሁለቱ ጥጆች ምንጭ ውሃ" ማለት ነው፤ አንዳንዶች ይህ ምንጭ የሚገኘው በስተ ምሥራቅ መፋሰሻ ነው ቢሉም፣ ከሙት ባሕር በስተ ሰሜን ምዕራብ በኩል ዳር ላይ የሚገኘው ዓይን ፈሽካ ሳይሆን አይቀርም::

47+11 *ጨው እንደሆነ ይቀራል፤* ምናልባት ለመሥዋዕት ስለሚያስፈልግ ሊሆን ይችላል (43+24)::

47+13 *ዮሴፍ ሁለት ዕጣ ይኑረው፤* የሌዊ ነገድ ምንም ድርሻ ስለማይኖረው፣ የዮሴፍ ሁለት ልጆች ኤፍሬምና ምናሴ ከያዕቆብ የልጅነት መብት ስላገኙ፣ (ዘፍ48+17-20) እያንዳን ዳቸው ርስታቸውን ተቀበሉ (48+4-5 ይመ)::

47+14 *ስለማልሁ፤* ለአብርሃም የገባውን ኪዳን የሚያመ ለክት ነው (ዘፍ15+9-21፤ ሕዝ20+5፤ 36+28 ይመ)::

47+15 *የምድሪቱ ወሰን ይህ ነው፤* ከዮርዳኖስ ማዶ ያለውን ምድር ሳይጨምር (ቍ18 ይመ)፣ በዳዊትና በሰሎሞን ዘመን የነበረውን የእስራኤል ወሰንን ከሞላ ጐደል ይይዛል:: ከዮርዳኖስ ማዶ ያለው ምድር በማንኛውም ሁኔታ ቢሆን በተስፋ ይቱ ምድር ክልል ውስጥ ሆኖ አያውቅም:: እዚህ ላይ በዝርዝር የተጠቀሱት የድንበር ወሰኖች በዘኍ34+1-12 ከተጠቀሱት ጋር ተመሳሳይ ናቸው:: *በሔትሎን መንገድ፤* በዛሬዪቱ ሊባኖስ ግዛት ውስጥ በሜዲትራንያን ባሕር ጠረፍ ላይ የምትገኝ ሳትሆን አትቀርም:: *በሐማት መተላለፊያ፤* አግራጭ ትርጕሙን ይመ፤ "መተላለፊያ" የሚለው ቃል ምናልባት፣ "መግቢያ" ሳይሆን ይች ላል፤ ነገር ግን ከሪብላ አጠገብ በኦሬንተስ ወንዝ ከቃዴስ በስተ ደቡብ ምዕራብ ሠላሳ ሁለት ኪሎ ሜትር ያህልና ከባልቤክ በስተ ሰሜን ምሥራቅ ሃያ አራት ኪሎ ሜትር ያህል የምትርቀው፣ የዛሬዪቱ ሌብዌ ሳትሆን አትቀርም፤ በአንድ ወቅት በስተ ደቡብ ሐማት መንገድ ላይ ሊቦ እንደ መጠበቂያ ምሽግ ሆና ስታገለግል ነበር:: ስለዚህ ይህ ሐረግ፣ "የሐማት መተላለፊያ" ተብሎ ሊተረጐም ይችላል:: በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ብዙ ጊዜ፣ የእስራኤል ሰሜናዊ ዳርቻ ወሰን እንደ ሆነ ተገልጾአል (ቍ20፤ 48+1፤ ዘኍ13+21፤ 34+8፤ ኢያ13+5፤ 1ነገ8+65፤ 2ነገ14+25፤ አሞ6+14 ይመ):: *ጽዳድ፤* በዘኍ34+8 ላይ ከመጠቀሱ በስተቀር ብዙም አይታወቅም::

47+16 *ቤሮታ፤* በ2ሳሙ8+8 ላይ የተጠቀሰችው ቤሮታይ ካልሆነች ስለ እርሷ የሚታወቅ የለም ማለት ነው:: *ደማስቆ፤* የአ ራም ወይም የሶርያ ዋና ከተማ ስትሆን፣ በቍ17 መሠረት በእስ ራኤል ግዛት ውስጥ የምትገኝ ናት:: *ሐማት፤* በኦሮንተስ ወንዝ ከደማስቆ በስተ ሰሜን አንድ መቶ ዘጠና ሁለት ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ የምትገኝ ከተማ ናት:: *ሲብራይም፤* የት ቦታ እንደምትገኝ አይታወቅም፤ ነገር ግን በ2ነገ17+24፤ 18+34 የተጠቀሰችው ሴፌርዋይም ልትሆን ትችላለች:: *ሐጸርሃቲኮን፤* "መካከለኛው ስፍራ" ማለት ነው፤ የት ቦታ እንደምትገኝ ባይታ ወቅም በቍ17 የተጠቀሰችው ሐጸር ዔናን ልትሆን ትችላለች::

በሰሜኑ የደማስቆ ድንበር አድርጎ፣ የሐማትንም ዳርቻ ወደ ሰሜን ትቶ እስከ ሐጸርዔናንም ይዘልቃል።

[18]"በምሥራቅ በኩል ወሰኑ በሐውራንና በደማስቆ መካከል፣ በገለዓድና በእስራኤል ምድር መካከል ዮርዳኖስ ይሆናል፤ የምሥራቁ ድንበር እስከ ምሥራቁ ባሕር ይወርድና እስከ ታማር° ይዘልቃል፤ ይህም የምሥራቁ ወሰን ይሆናል።

[19]"በደቡብ በኩል ወሰኑ ከታማር ይነሣና እስከ ሜሪባ ቃዴስ ውሃ ይደርሳል፤ ከዚያም የግብፅን ደረቅ ወንዝ ተከትሎ እስከ ታላቁ ባሕር ይዘልቃል፤ ይህ የደቡቡ ወሰን ነው።

[20]"በምዕራቡ በኩል ወሰኑ ከሐማት መግቢያ ፊት ለፊት እስካለው ቦታ ድረስ ታላቁ ባሕር ይሆናል፤ ይህም የምዕራቡ ወሰን ይሆናል።

[21]"እንሆ፤ ይህችን ምድር በእስራኤል ነገድ ቍጥር ልክ ትከፋፈላላችሁ፤ [22]ለራሳችሁ፣ በመካከላችሁ ለሚኖሩት ልጆች ላሏቸው መጻተኞች ርስት አድርጋችሁ መድቡ፤ እነርሱንም እንደ እስራኤል ተወላጆች ቍጠሯቸው፤ እንደ እናንተ ከእስራኤል ነገዶች ርስት ይመደብላቸው። [23]መጻተኛ በማንኛውም ነገድ መካከል ቢቀመጥ፣ በዚያ ርስቱን ስጡት" ይላል ጌታ እግዚአብሔር።

### የምድሪቱ አከፋፈል

**48** "ስማቸው የተዘረዘረው ነገዶች እነዚህ ናቸው፤ በሰሜኑ ድንበር የዳን ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የሔትሎንን መንገድ ተከትሎ እስከ ሐማት መተላለፊያ ይደርሳል። ሐጸርዔናንና ከሐማት ቀጥሎ ያለው የደማስቆ ሰሜናዊ ድንበር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ላለው ወሰኑ አንድ ክፍል ይሆናል።

[2]"የአሴር ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የዳንን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[3]"የንፍታሌም ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የአሴርን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[4]"የምናሴ ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የንፍታሌምን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[5]"የኤፍሬም ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የምናሴን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[6]"የሮቤል ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የኤፍሬምን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[7]"የይሁዳ ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የሮቤልን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[8]"ይሁዳን ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ የሚያዋስነው ምድር ለመባ የሚቀርብ ድርሻ ይሆናል፤ ስፋቱም ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ነው፤ ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያለውም ርዝመቱ፣ ከነገዶቹ ድርሻ እንደ አንዱ ሆኖ፣ መቅደሱ በመካከሉ ይሆናል።

[9]"*ለእግዚአብሔር* የምታቀርቡት የዚህ መባ ርዝመት ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ሲሆን፣ ስፋቱ ዐሥር ሺህ ክንድ ይሆናል። [10]ይህ ለካህናቱ የተቀደሰ ድርሻ ይሆናል፤ በሰሜን በኩል ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ፣ በምዕራብ በኩል ወርዱ ዐሥር ሺህ ክንድ በምሥራቅ በኩል ወርዱ ዐሥር ሺህ ክንድ ሲሆን በደቡብ በኩል ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ይሆናል፤ *የእግዚአብሔርም* መቅደስ በመካከሉ ይቆማል። [11]ይህም እስራኤላውያን በሳቱ ጊዜ፣ እንደ ሳቱት ሌዋውያን ሳይስቱ ለቀሩት፣ በታማኝነት ሳገለገሉኝ ለተቀደሱት ካህናት ለሳ

°17 በዕብራይስጥ ዔኖን የዔናን አማራጭ ትርጕም ነው
°18 ሰብዓ ሊቃናትና ሱርስት እንዲሁ ሲሆኑ ዕብራይስጡ ግን *እስራኤል ባሕሩን በምሥራቅ በኩል ትለካለህ፤ ይላል*

47+18 ሕዝ27+18
47+19 ቍ15፤ ዘፍ 15+18፤ ዘዳ32+51፤ ኢሳ27+12፤ ሕዝ 48+28
47+20 ዘኍ13+21፤ 34+6፤ሕዝ48+1
47+22 ዘሌ24+22፤ ዘኍ15+29፤26+55-56፤ዘዳ24+19፤ ኢሳ14+1፤56+6-7፤ ሕዝ36+12፤ ሚል3+5፤ ሮሜ10+12፤ ኤፌ 2+12-16፤3+6፤ ቈላ 3+11
47+23 ዘዳ10+19
48+1 ዘፍ30+6፤ ሕዝ47+15-17፡20
48+2 ኢያ19+24-31
48+3 ኢያ19+32-39
48+4 ኢያ17+1-11
48+5 ኢያ16+5-9፤17+7-10፡17
48+6 ኢያ13+15-21
48+7 ኢያ15+1-63
48+8 ቍ21
48+9 ሕዝ45+1
48+10 ቍ21፤ ሕዝ 45+3-4
48+11 ዘሌ8+35፤ 2ሳሙ8+17፤ ሕዝ14+11፤44+15

47+18 *እስከ ምሥራቁ ባሕር፤* ሙት ባሕር ነው (ኢል 2+20፤ ዘካ14+8 ይመ)። *ታማር፤* "የታምር ቦታ" ማለት ነው (ቍ19፤ 48+28 ይመ)፤ በዘፍ14+7 (ሐሴሶን ታማር)፣ በ1ነገ 9+18 (አማራጭ ትርጕሙን ይመ)፤ ይህ ስፍራ ከዓይን ጋዲ እንደሆነ በ2ዜና20+2 ተገልጾአል (የቍ10 ማብ ይመ)።

47+19 *ሜሪባ ቃዴስ፤* ከቤርሳቤህ በስተ ደቡብ ሰማንያ ኪሎ ሜትር ርቀር ላይ የምትገኝ ወረዳ ስትሆን፣ በዘኍ34+4 ላይም ከቃዴስ በርኔ እንደምትገኝ ተገልጾአል። *የግብፅ ደረቅ ወንዝ፤* ከሰሜን ሲና፣ እስከ ሰሜን ምዕራብ ሜዲትራንያን ባሕር መፋሰሻ ድረስ ሰማንያ ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ የሚገኝና ጥልቅ የሆነ ከክረምት በስተቀር ውሃ የማይገኝበት ሸለቆ ነው፤ የሰሎሞን መንግሥት ግዛት ደቡባዊ ጫፍም ይዋሰነዋል (1ነገ8+65)።

47+22 *እነርሱንም እንደ እስራኤል ተወላጆች ቍጠሯቸው፤* ይህ በ14+7 ላይ ከተጻፈው ይልቅ ብልጫ ያለው የቸርነት ሥራ ነው፤ በኢሳ56+3-8 ላይ ከተገለጸው ጋር አንድ ዐይነት የሆነ የእግዚአብሔርን ሁለንታዊ የቸርነት ሥራ የሚያንጸባርቅ ነው።

48+1 *ዳን፤* የእስራኤልን መንግሥት ግዛት ወሰን በተመለከተ፣ "ከዳን እስከ ቤርሳቤህ" እየተባለ በታሪክ ሲጠቀስ የኖረውን (ለምሳሌ መሳ20+1፤ 1ሳሙ3+20 ይመ)፤ የሰሜኑን ጫፍ ዳር ድንበር ክፍል ይህ ነገድ በርስትነት ይይዛል። "ዳን" ከራሔል አገልጋይ ከባላ የተወለደ ነበር (ዘፍ35+25)። *ሔትሎን ... እስከ ሐማት መተላለፊያ፤* የ47+15 ማብ ይመ። *ሐጸርዔናን፤* የ47+16 ማብ ይመ።

48+2 *አሴር፤* ከልያ አገልጋይ ከዘለፋ የተወለደ ነው (ዘፍ 35+26)፤ ያዕቆብ ከሚስቶቹ አገልጋዮች የወለዳቸው ልጆች ዝርያዎች የያዙት ርስት መቅደሱ ካለበት ቦታ ራቅ ብሎ የሚገኝ ነው (ዳን ቍ1፤ ንፍታሌም ቍ3፤ ጋድ ቍ27 ይመ)።

48+3 *ንፍታሌም፤* ከራሔል አገልጋይ ከባላ የተወለደ ነው (የቍ2 ማብ ይመ)።

48+4 *ምናሴ፤* የ47+13 ማብ ይመ።

48+5 *ኤፍሬም፤* የ47+13 ማብ ይመ።

48+6 *ሮቤል፤* የልያ የበኵር ልጅ ነው (ዘፍ29+31)።

48+7 *ይሁዳ፤* የልያ ልጅ ነው (ዘፍ35+23)። በመካከል ያለውን የተቀደሰውን ስፍራ የሚያዋስን ነው (ቍ8)፤ ለእርሱም ከሁሉ የተሻለ ርስት ተሰጥቶታል፤ ምክንያቱም የመሲሑ የመምጣቱ ተስፋ ለዚህ ነገድ ስለ ተነገረ ነው (ዘፍ49+8-12)።

*48+8-22፤* በ45+1-8 ላይ የተገለጸውን ሐሳብ በዝርዝር የያዘ ነው።

48+9 *ስፋቱም ዐሥር ሺህ ክንድ፤* የተቀደሰው ስፍራ አጠቃላይ ስፋት፣ ሃያ ሺህ ክንድ ነበረ (45+1 ይመ)። ይህ ለካህናቱ ወይም ለሌዋውያኑ የተሰጠውን ቦታ ስፋት የሚያመለክት ነው። የሰባ ሊቃናት ትርጕም ስፋቱን "ሃያ ሺህ" ብሎታል።

48+11 *በታማኝነት ሳገለገሉኝ ...ለሳዶቃውያን፤* የ44+15 ማብ ይመ።

ዶቃውያን ይሆናል። [12]የሌዋውያንን ምድር ከሚያዋስነው፣ ከምድሪቱ ቅዱስ ድርሻ እጅግ የተቀደሰው ድርሻ ለእነርሱ ልዩ ስጦታ ይሆናል።

[13]"ከካህናቱም ምድር ጐን ለጐን ሌዋውያኑ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ርዝመትና ዐሥር ሺህ ክንድ ወርድ ያለው ይዞታ ይኖራቸዋል፤ ጠቅላላ ርዝመቱ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ፣ ወርዱም ዐሥር ሺህ ክንድ ይሆናል። [14]ከዚህ ላይ መሸጥ ወይም መለወጥ የለባቸውም። ይህ ከምድሪቱ ሁሉ ምርጥ ስለ ሆነ፣ ወደ ሌላ እጅ አይተላለፍም፤ ለእግዚአብሔር የተቀደሰ ነውና።

[15]"አምስት ሺህ ክንድ ወርድና ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ርዝመት ያለው የቀረው ቦታ ለከተማዪቱ የጋራ ጥቅም፣ ለቤት ሥራና ለከብት ማሰማሪያ ይውላል፤ ከተማዪቱም በመካከሉ ትሆናለች፤ [16]የከተማዪቱም መጠን በሰሜን አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ፣ በደቡብ አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ፣ በምሥራቅ አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ፣ የምዕራቡም እንዲሁ አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ ይሆናል። [17]የከተማዪቱ ከብት ማሰማሪያ ቦታ፣ በሰሜን ሁለት መቶ አምሳ ክንድ፣ በደቡብ ሁለት መቶ አምሳ ክንድ፣ በምሥራቅ ሁለት መቶ አምሳ ክንድ፣ በምዕራብም ሁለት መቶ አምሳ ክንድ ይሆናል። [18]ከዚህ የሚቀረው፣ የተቀደሰውን ክፍል የሚያዋስነውና በተጓዳኝ ያለው ቦታ በምሥራቅ ዐሥር ሺህ ክንድ፣ በምዕራብ ዐሥር ሺህ ክንድ ይሆናል። ምርቱም ለከተማዪቱ ሠራተኞች ምግብ ይሆናል። [19]ምድሪቱን የሚያርሱ የከተማዪቱ ሠራተኞች ከሁሉም ነገዶች ይመጣሉ። [20]አጠቃላይ ይዞታው በአራቱም ማእዘን እኩል ሲሆን፣ እያንዳንዱ ማእዘን ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ነው፤ ከከተማዪቱ ድርሻ ጋር የተቀደሰውን ክፍል ልዩ መባ በማድረግ ታስቀምጣላችሁ።

[21]"በተቀደሰው ድርሻና በከተማዪቱ ቦታ ግራና ቀኝ ያለው ቀሪ ቦታ፣ ለገዢ ይሆናል፤ ይህም ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ከሆነው ከተቀደሰው ቦታ አንሥቶ በምሥራቅ በኩል እስከ ምሥራቁ ወሰን ይዘልቃል፤ በምዕራቡም በኩል እንዲሁ ሃያ አምስት ሺህ ክንድ ከሆነው ይዞታ አንሥቶ እስከ ምዕራቡ ወሰን ይዘልቃል። የየነገዱ ድርሻ ከሆነውም መሬት ጐን ለጐን የሚሄዱት ቦታዎች የገዢ ይሆናሉ። የተቀደሰው ቦታና መቅደሱ በመካከላቸው ይሆናሉ። [22]ስለዚህ የሌዋውያኑ ይዞታና የከተማዪቱ ይዞታ ለገዢ በተሰጠው ቦታ መካከል ይሆናል፤ የገዢ ቦታም በይሁዳ ድንበርና በብንያም ድንበር መካከል ይሆናል።

[23]"የቀሩት ነገዶች ድርሻ እንደሚከተለው ይሆናል፤ 'ብንያም ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ይዘልቃል።

[24]'የስምዖን ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የብንያምን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[25]'የይሳኮር ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የስምዖንን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[26]'የዛብሎን ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የይሳኮርን ምድር ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[27]'የጋድ ነገድ አንድ ድርሻ ይኖረዋል፤ ይህም የዛብሎንን ግዛት ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያዋስናል።

[28]'የጋድ ደቡባዊ ወሰን ከታማር ደቡብ እስከ ሜሪባ ቃዴስ ውሃዎች ይደርሳል፤ የግብፅን ደረቅ ወንዝ ይዞ እስከ ታላቁ ባሕር* ይዘልቃል።

[29]'ለእስራኤል ነገዶች ርስት አድርጋችሁ የምታከፋፍሏት ምድር ይህች ናት፤ ድርሻዎቻቸውም እነዚህ ናቸው" ይላል ጌታ እግዚአብሔር።

### የከተማዪቱ በሮች

[30]'የከተማዪቱ መውጫ በሮች እነዚህ ናቸው፤ ከሰሜን በኩል አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ ርዝመት ካለው በር አንሥቶ፣ [31]የከተማዪቱ በሮች በእስራኤል ነገዶች ስም ይጠራሉ፤ በሰሜን በኩል ያሉት ሦስቱ በሮች የሮቤል ነገድ በር፣ የይሁዳ ነገድ በርና የሌዊ ነገድ በር ይሆናሉ።

[32]'በምሥራቅ በኩል አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ ርዝመት ባለው በር ሦስት በሮች ይኖራሉ፤ እነዚህም የዮሴፍ በር፣ የብንያም በርና የዳን በር ናቸው።

[33]'በደቡብ በኩል አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ ርዝመት ባለው በር ሦስት በሮች አሉ፤ እነዚህም የስምዖን በር፣ የይሳኮር በርና የዛብሎን በር ናቸው።

[34]'በምዕራብ በኩል አራት ሺህ አምስት መቶ ክንድ ርዝመት ባለው በር ሦስት

48፥13 ሕዝ45፥5
48፥14 ዘሌ25፥34፤ 27፥10፡28
48፥16 ራእ21፥16
48፥18 ሕዝ45፥6
48፥21 ቍ8፡10፤ ሕዝ45፥7
48፥23 ኢያ18፥11-28
48፥24 ዘፍ29፥33፤ ኢያ19፥1-9
48፥25 ኢያ19፥17-23
48፥26 ኢያ19፥10-16
48፥27 ኢያ13፥24-28
48፥28 ዘፍ14፥7፤ ዘኍ34፥6፤ ሕዝ 47፥19
48፥29 ሕዝ45፥1
48፥34 2ዜና4፥4፤ ራእ21፥12-13

*28 ሜድትራኒያንን ያመለክታል

48፥14 *መሸጥ ወይም መለወጥ፤* የእግዚአብሔር ሀብት ስለ ሆነ ለንግድ የሚውል አይደለም።

48፥19 *ከሁሉም ነገዶች፤* የተቀደሰው ስፍራ የራሱ የሕዝቡ ብሔራዊ ሀብት እንጂ፣ የገዥው የግል ርስት አይደለም።

48፥23 *ብንያም፤* የራሔል ልጅ ነው (ዘፍ35፥24)።

48፥24 *ስምዖን፤* የልያ ልጅ ነው (ዘፍ35፥23)።

48፥25 *ይሳኮር፤* የልያ ልጅ ነው (ዘፍ35፥23)።

48፥26 *ዛብሎን፤* የልያ ልጅ ነው (ዘፍ35፥23)።

48፥27 *ጋድ፤* የልያ ባሪያ የዘለፋ ልጅ ነው (የቍ2 ማብ ይመ)።

48፥28 *ታማር፤* የ47፥18 ማብ ይመ። *መሪባ ቃዴስ፤* የ47፥19 ማብ ይመ። *የግብፅን ደረቅ ወንዝ፤* የ47፥19 ማብ ይመ።

48፥31 *የሮቤል ... የይሁዳ ... የሌዊ፤* እነዚህ እጅግ በጣም የታወቁት ነገዶች፦ በኵሩ ሮቤል፣ የመሲሑ ነገድ ይሁዳ፣ ሌዊ፣ የካህናት ነገድ መገኛ፣ ናቸው፤ እነርሱም በአንድነት በሰሜን በኩል በሮች አሏቸው። በዚህ ዝርዝር ሌዊ ስለተጨመረ፣ የሴፍ (ቍ32) ኤፍሬምንና ምናሴን በመወከል፣ የእስራኤልን ነገድ ቍጥር ዐሥራ ሁለት ያደርገዋል፣ በሮቹን በተመለከተ ከራእ21፥12-14 ጋር ያነጻጽሩ።

በሮች ይኖራሉ፤ እነዚህም የጋድ በር፣ የአሴር በርና የንፍታሌም በር ናቸው።
[35]" 'የከተማዪቱም ዙሪያ ዐሥራ ስምንት ሺህ ክንድ ይሆናል፤
" 'የከተማዪቱ ስም፣ ከዚያን ጊዜ ጀምሮ "እግዚአብሔር በዚያ አለ" ይሆናል።' "

48፥35 ኢሳ12፥6፤ 24፥23፤ኤር3፥17፤ 14፥9፤ኢል3፥21፤ ራእ 3፥12፤21፥3

48፥35 *እግዚአብሔር በዚያ አለ፤* ቅድስቲቱን ከተማ በተመለከተ ይህ ወሳኝ ኀይለ ቃል ነው፤ በዕብራይስጡ፣ "ያህዌ ሻማ" የሚለው ቃል፣ "የሩሻሌም" ከሚለው ቃል ጋር ተመሳሳይ ድምፀት የሚሰጠው ነው። የኢየሩሳሌምን ሌሎች ስሞች በተመለከተ 23፥4፤ ኢሳ1፥26፤ 60፥14፤ 62፥2-4፡12፤ ኤር3፥17፤ 33፥16፤ ዘካ8፥3 ይመ።

# ትንቢተ ዳንኤል

## መግቢያ

### ጸሐፊው፣ የተጻፈበት የመጽሐፉ እውነተኛነት

ጸሐፊው ዳንኤል እንደ ሆነ መጽሐፉ ራሱ ብዙ ቦታ ላይ ይገልጻል፤ ለምሳሌ ያህል 9፥2 እና 10፥2 ላይ ተጠቅሶ እናያለን:: ጌታ ኢየሱስ በዚህ ነጥብ የሚስማማ መሆኑን፣ "እንግዲህ በነቢዩ በዳንኤል የተባለውን 'የጥፋት ርኵሰት'..." በማለቱ ከ9፥27፤ ከ11፥31፤ ከ12፥11 ላይ መጥቀሱን እንረዳለን (ማቴ 24፥15):: መጽሐፉ ተጽፎ ያለቀው ቂሮስ በ539 ዓ.ቅ.ክ. ባቢሎንን ከማረከ በኋላ ብዙም ሳይቈይ በ530 ዓ.ቅ.ክ. ገደማ ሳይሆን አይቀርም::

የትንቢተ ዳንኤል አብዛኛው ክፍል ልብ ወለድ መጽሐፍ ነው የሚሉ አሉ፤ ይኸውም ጊዜው ይህን ያህል ሰፊ ዘመን ባካተተ ጉዳይ ላይ ትንቢት መናገር አይቻልም ከሚል እንጉል ዘመናዊ ፍልስፍና የመጣ ስሕተት ነው:: ስለዚህ በዳንኤል ትንቢት መሠረት ስለ ተፈጸሙ ሁኔታዎች ሁሉ የተጻፈው ከመቃብያን ዘመን (ከሁለተኛው ምእተ ዓ.ቅ.ክ.) ቀደም ሲል መሆን አይችልም ይላሉ፤ ይህም ማለት ደግሞ መጽሐፉ የተጻፈው ተነገረ የተባለው ትንቢት መፈጸም ከጀመረ በኋላ ነው ማለት ነው:: ነገር ግን ተጨባጩ ማስረጃ ይህን መሠረት የለሽ ግንዛቤ በብዙ መንገድ ይሽረዋል:- (1) ትንቢተ ዳንኤል የተጻፈው በኋለኛው ዘመን እንደ ሆነ የሚያምኑት በመጽሐፉ ውስጥ የተጠቀሰውን ይህን ያህል ሰፊ ዘመን ያካተተውን ትንቢት ፍጻሜ ለማስወገድ በም 2 እና 7 ላይ የተጠቀሱትን አራቱን መንግሥታት ማለት የባቢሎን፣ የሜዶን የፋርስና የግሪክ መንግሥታት እንደ ሆኑ ይናገራሉ:: ነገር ግን በጸሐፊው አመለካከት "ሜዶንና ፋርስ" በጥምር (5፥28) በአራቱ መንግሥታት ዝርዝር ውስጥ (2፥36-43) እንደ ሁለተኛ መንግሥታት የሚታዩ ናቸው:: ስለዚህ አራቱ መንግሥት የባቢሎን፣ የሜዶን-ፋርስ፣ የግሪክና የሮም መንግሥታት መሆናቸው ግልጽ ነው::

(2) የጽሑፉ የቋንቋ አጠቃቀም ራሱ መጽሐፉ ከሁለተኛው (ምእተ ዓ.ቅ.ክ.) ቀደም ብሎ እንደ ተጻፈ የሚያመለክት ነው:: በሁለተኛው ምእተ ዓ.ቅ.ክ. ላይ የነበረው የዕብራይስጥና የአረማይክ ቋንቋ ምን ቅርጽና ይዘት እንደ ነበረው ከሙት ባሕር ከተገኙት የብራና ጥቅልል ጽሑፎች ከብዙ በጥቂቱ መረዳት ይቻላል፤ በመሆኑም በትንቢተ ዳንኤል ላይ የሚገኙት በዕብራይስጥና በአረማይክ ቋንቋ የተጻፉት ምዕራፎች ከሁለተኛው ምእተ ዓ.ቅ.ክ. ዓመታት ቀደም ብለው እንደ ተጻፉ ከዚህ ጋር በማነጻጸር መገንዘብ ይቻላል:: ከዚህም በላይ በትንቢተ ዳንኤል ውስጥ የሚገኙት የፋርስና የግሪክ ቃላት የቅርብ ጊዜ ቋንቋ ሊሆኑ አይችሉም:: በምዕራፍ ሦስት ላይ የሚገኙት አንዳንድ ቃላት በሁለተኛው ምዕተ ዓ.ቅ.ክ ቀድሞውኑ ከጥቅም ውጭ ሆነው ስለነበር፣ ሰብዓ ሊቃናት ብሉይ ኪዳንን ወደ ግሪክ ቋንቋ በተረጐሙበት ጊዜ በዚህ ረገድ ተሳስተዋል::

(3) በዳንኤል ከተነገሩት ትንቢቶች ብዙዎቹ በሁለተኛው ምእተ ዓ.ቅ.ክ. ላይ አልተፈጸሙም በማለት ብቻ ትንቢትነቱን መሻር አይቻልም:: የአራተኛው መንግሥት ምሳሌ ሆኖ የቀረበው ምልክት ስለ ሮም መንግሥት አስቀድሞ የተነገረ መሆኑ ከቶ አያጠራጥርምና (2፥33፤ 7፥7:9 ይመ)፤ የሮም መንግሥት እስከ 63 ዓ.ቅ.ክ. ድረስ ሶርያንና መካከለኛውን ምሥራቅ አልተቈጣጠረም:: ስለ "መሲሑ ገዥ" የተነገረው ትንቢትም "ኢየሩሳሌምን ለመጠገንና ለመሥራት ትእዛዝ ከወጣ" (9፥25)፣ ከአራት መቶ ስማንያ ሦስት ዓመት በኋላ፣ ከጌታ ኢየሱስ የአገልግሎት ዘመን ጋር በትክክል ይገጥማል::

ስለዚህ መጽሐፉ የተጻፈው ወደ ኋለኛው ዘመን ላይ ነው የሚለውን ግምት ተጨባጩ ማስረጃ ይሽረዋል፤ መጽሐፉን የጻፈው ዳንኤል አይደለም የሚለውንም አባባል ያለ በቂ ምክንያት የተሰነዘረ ያደርገዋል::

### የመጽሐፉ መሪ ሐሳብ

የመጽሐፉ ትምህርተ መለኮታዊ መሪ ሐሳብ "የእግዚአብሔር ሉዓላዊነት" ነው፤ "ልዑል አምላክ በሰዎች መንግሥት ላይ ሥልጣን እንዳለው..." (5፥21) ይገልጣል:: ለዳንኤል የተገለጡ ራእዮች ምን ጊዜም የእግዚአብሔርን አሸናፊነት የሚያሳዩ ናቸው (7፥11:26-27፤ 8፥25፤ 9፥27፤ 11፥45፤ 12፥13):: ሉዓላዊነቱ ከሁሉ በላይ ጐልቶ የተገለጠው በዮሐንስ ራእይ መጽሐፍ ውስጥ ነው፤ "የዓለም መንግሥት ለጌታችንና ለክርስቶስ ሆነች፤ ለዘላለም እስከ ዘላለም ይነግሣል" (ራእ 11፥15 እና ዳን 2፥44፤ 7፥27 ያነጻጽሩ)::

### የሥነ ጽሑፉ ገጽታ

በመሠረቱ ይህ መጽሐፍ ታሪክ ነክና (በአብዛኛው ም 1-6 ላይ የሚገኝ) ራእይ ነክ (በአብዛኛው ም7-12 ላይ የሚገኝ) አጻጻፍ ይዟል:: ራእይ ነክ የተባለው ክፍል ትእምርታት፣ የመገለጥ ራእይና ትንቢታዊ ሥነ ጽሑፍ የሞላበት ሲሆን፣ በአስጨናቂ ወቅት የተጻፈና በትምህርተ መለኮት ይዘቱ አብዛኛው ስለ ዘመናት ፍጻሜ የሚተርክ ነው:: ራእይ ነክ ጽሑፍ በመሠረቱ የእግዚአብሔርን ሕዝብ የሚያበረታታ ነው (በትንቢተ ዘካርያስ መግቢያ ውስጥ፣ 'የሥነ ጽሑፍ ገጽታ' የሚለውን ርእስ ይመ፤ በተጨማሪም በዮሐንስ ራእይ መግቢያ፣ 'የሥነ ጽሑፍ ገጽታ' የሚለውን ርእስ ይመ):: በራእይ ነክ ጽሑፍ ውስጥ ስለ ቍጥሮች ትእምርታዊ (አመልካችነት) አጠቃቀም በዮሐንስ ራእይ መግቢያ፣ "ልዩ ገጽታ"

በሚለው ርእስ ሥር የተጻፈውን ይመ።

**አስተዋጽኦ**

1. መግቢያ፤ መቼት (ም 1፤ በዕብራይስጥ)
    - ሀ. ታሪካዊ መግቢያ (1፥1-2)
    - ለ. ዳንኤልና ባልንጀሮቹ ተማርከው ሄዱ (1፥3-7)
    - ሐ. ወጣቶቹ በእምነታቸው ጸንተው ተገኙ (1፥8-16)
    - መ. ወጣቶቹ ለከፍተኛ ሥልጣን በቁ (1፥17-21)
2. የዓለም መንግሥታት ዕጣ ፈንታ (ም 2-7፤ በአራማይክ ቋንቋ ከ2፥4 አጋማሽ ጀምሮ)
    - ሀ. ናቡከደነፆር በሕልሙ ያየው ምስል (ም 2)
    - ለ. ናቡከደነፆር የወርቅ ምስል ማሠራቱና እንዲመለክ ማዘዙ (ም 3)
    - ሐ. ናቡከደነፆር በሕልሙ አንድ ግዙፍ ዛፍ አየ (ም 4)
    - መ. የንጉሥ ብልጣሶርና የባቢሎን ውድቀት ተገለጠ (ም 5)
    - ሠ. እግዚአብሔር ዳንኤልን ከአንበሶች አፍ አዳነው (ም 6)
    - ረ. ዳንኤል በሕልሙ አራት አውሬዎችን አየ (ም 7)
3. የእስራኤል መንግሥት ዕጣ ፈንታ (ም 8-12፤ በዕብራይስጥ ቋንቋ)
    - ሀ. ዳንኤል በራእዩ ያያቸው አንድ አውራ በግና አንድ አውራ ፍየል (ም 8)
    - ለ. የዳንኤል ጸሎትና በራእዩ ያያቸው ሰባ “ሳምንቶች” ራእይ (ም 9)
    - ሐ. ዳንኤል ስለ እስራኤል የወደፊት ሁኔታ ያየው ራእይ (ም 10-12)
        - (1) ወደ ፊት ስለሚሆኑ ነገሮች ያየው ራእይ (10፥1-3)
        - (2) በመልአኩ በኩል የተቀበለው ራእይ (10፥4-11፥1)
        - (3) ስለ ፋርስና ስለ ግሪክ የተነገሩ ትንቢቶች (11፥2-4)
        - (4) ስለ ግብፅና ስለ ሶርያ የተነገሩ ትንቢቶች (11፥5-35)
        - (5) ስለ ሐሰተኛው ክርስቶስ የተነገሩ ትንቢቶች (11፥36-45)
        - (6) መከራና ትድግና (12፥1)
        - (7) የሙታን ትንሣኤ (12፥2-3)
        - (8) ለዳንኤል የተሰጠ መመሪያ (12፥4)
        - (9) መደምደሚያ (12፥5-13)

## ዳንኤል በባቢሎን እንዲሠለጥን ተደረገ

**1** የይሁዳ ንጉሥ ኢዮአቄም በነገሠ በሦስተኛው ዓመት የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር ወደ ኢየሩሳሌም መጥቶ ከበባት። [2]ጌታም የይሁዳን ንጉሥ ኢዮአቄምን በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ካሉት ዕቃዎች ከጥቂቶቹ ጋር በእጁ አሳልፎ ሰጠው፤ ወደ አምላኩ ቤት ወደ ባቢሎን[ሀ] ወሰዳቸው፤ በአምላኩም ግምጃ ቤት ውስጥ አኖራቸው።

[3]ከዚያ በኋላ ንጉሡ የቤተ መንግሥቱን ጃንደረቦች አለቃ አስፋኔዝን፣ ከንጉሣዊው ቤተ ሰብና ከመሳፍንቱ ዘር የሆኑትን እስራኤላውያንን እንዲያመጣ አዘዘው፤ [4]እነርሱም የአካል ጕዳት የሌለባቸው መልከ መልካሞች፣ ማንኛውንም ትምህርት የመማር ችሎታ ያላቸው፣ ዕውቀት የሞላባቸው፣ ሁሉን ነገር በፍጥነት መረዳት የሚችሉትንና በንጉሡም ቤት ለማገልገል ብቃት ያላቸው ወጣት ወንዶች ናቸው፤ የባቢሎናውያንንም[ለ] ቋንቋና ሥነ ጽሑፍ እንዲያስተምራቸው አዘዘው። [5]ንጉሡም በየዕለቱ የሚበሉትን ምግብና የሚጠጡትን የወይን ጠጅ ከንጉሡ ማእድ ድርሻ እንዲሰጣቸው አደረገ፤ ለሦስት ዓመት ከሠለጠኑ በኋላ በንጉሡ አገልግሎት ላይ የሚሰማሩ ናቸው።

[6]ከነዚህም መካከል ከይሁዳ የመጡት ዳንኤል፣ አናንያ፣ ሚሳኤልና አዛርያ ነበሩ፤ [7]የጃንደረቦቹ አለቃም አዲስ ስም አወጣላቸው፤ ዳንኤልን ብልጣሶር፣ አናንያን ሲድራቅ፤ ሚሳኤልን ሚሳቅ፣ አዛርያን አብድናጎ ብሎ ጠራቸው።

[8]ዳንኤል ግን በንጉሡ ምግብና የወይን ጠጅ እንዳይረክስ ወሰነ፤ በዚህ መንገድ ራሱን እንዳያረክስም የጃንደረቦቹን አለቃ ፈቃድ ጠየቀው። [9]እግዚአብሔርም ለዳንኤል በጃንደረቦቹ አለቃ ፊት ሞገስንና መወደድን ሰጠው። [10]ሆኖም የጃንደረቦቹ አለቃ ለዳንኤል፣ "መብሉንና መጠጡን የመደበላችሁን ጌታዬን ንጉሡን እፈራለሁ፤ በዕድሜ እንደ እናንተ ካሉ ወጣቶች ይልቅ ከሲታችሁ ብትታዩ፣ በንጉሡ ዘንድ በራሴ ላይ አደጋ ታስከትሉብኛላችሁ።" ብሎ ነገረው።

[11]ዳንኤልም የጃንደረቦቹን አለቃ በዳንኤል፣ በአናንያ፣ በሚሳኤልና በአዛርያስ ላይ የሾመውን መጋቢ እንዲህ አለው፤ [12]"እባክህ አገልጋዮችህን ለዐሥር ቀን ያህል ፈትነን፤ ለመብል ከአትክልት፣ ለመጠጥም ከውሃ በስተቀር ምንም አይሰጠን፣ [13]ከዚያም የእኛን መልክና የንጉሡን መብል የሚበሉትን ወጣቶች መልክ አስተያይ፤ በአገልጋዮችህ ላይ የወደድኸውን አድርግብን።" [14]እርሱም በዚህ ነገር ተስማማ፤ ለዐሥር ቀንም ፈተናቸው።

[15]ከዐሥር ቀን በኋላም የንጉሡን መብል ከበሉት ከሌሎች ወጣቶች ይልቅ ጤናማዎችና ሰውነታቸው የወፈረ ሆነው ተገኙ። [16]ስለዚህ መጋቢው ምርጥ የሆነውን ምግባቸውንና ሊጠጡት የሚገባውን የወይን ጠጅ አስቀርቶ በምትኩ አትክልት ሰጣቸው።

[17]እግዚአብሔር ለእነዚህ አራት ወጣቶች በማንኛውም ሥነ ጽሑፍና ትምህርት ዕውቀትንና ማስተዋልን ሰጣቸው፣ ዳንኤልም ማንኛውንም ራእይና ሕልም የመረዳት ችሎታ ነበረው።

[18]ወደ እርሱ እንዲመጡ ንጉሡ የወሰነው ጊዜ ሲደርስ፣ የጃንደረቦቹ አለቃ ወደ ናቡከደነፆር አቀረባቸው፤ [19]ንጉሡም ባነጋገራቸው ጊዜ ከመካከላቸው እንደ ዳንኤል፣ አናንያ፣ ሚሳኤልና አዛርያ ያለ ከቶ አልተገኘም፤ ስለዚህ በንጉሡ አገልግሎት ላይ ተሰማሩ። [20]ንጉሡ በጠየቃቸው በማንኛውም የጥበብና የማስተዋል ጕዳይ በመላ ግዛቱ ካሉት አስማተኞችና ድግምተኞች ሁሉ ዐሥር እጅ

1፥1 2ነገ24፥1፤2ዜና 36፥6፤ኤር28፥14፤ 35፥11፤46፥2፤50፥1
1፥2 2ነገ24፥13፤2ዜና 36፥7፤ኤር27፥19-20፤ ዘካ5፥5-11
1፥3 2ነገ20፥18፤ 24፥15፤ኢሳ39፥7
1፥4 ቍ17፤ዘፍ3 9፥6፤ ዕዝ4፥7
1፥5 ቍ8፡10፡ 18፡19፤ አስ2፥5-6፡9
1፥6 ሕዝ14፥14፤ ዳን 2፥17፡25
1፥7 ኢሳ39፥7፤ ዳን 2፥26፡49፤ 3፥12፤4፥8፤5፥12፤10፥1
1፥8 ሕዝ4፥13-14
1፥9 ዘፍ39፥21፤ 1ነገ8፥50፤ ምሳ16፥7
1፥10 ቍ5
1፥12 ራእ2፥10
1፥13 ቍ16
1፥14 ራእ2፥10
1፥15 ዘፀ23፥25
1፥16 ቍ12-13
1፥17 ኢዮ12፥13፤ ዳን2፥19፡23፡30፤5፥1 1፡7፥1፤8፥1፤ቈላ1፥9፤ ያዕ1፥5
1፥18 ቍ5
1፥19 ዘፍ41፥46
1፥20 ዘፍ41፥8፤1ነገ 4፥30፤አስ2፥15፤ሕዝ 28፥3፤ዳን2፥13፡28፤ 4፥18፤6፥3

[ሀ]2 ዕብራይስጡ ሺናር ይላል
[ለ]4 ወይም ከለዳውያን

1፥1 *በሦስተኛው ዓመት፤* ኢዮአቄም በ608 ዓ.ቅ.ክ የነገሠበት የመጀመሪያው ዓመት የዋለው በአዲሱ ዓመት መጀመሪያ ላይ ነበር፤ በባቢሎናውያን የንግሥና ዘመን አቈጣጠር መሠረት የኢዮአቄም ሦስተኛው ዓመት የዋለው በ605 ዓ.ቅ.ክ ነው። የንግሥና ዘመን ራሱ እንደ መጀመሪያ ዓመት በሚቈጠርበት በአይሁድ የአቈጣጠር ሥርዐት መሠረት ግን፣ ይህ ወቅት የንጉሡ አራተኛው የንግሥና ዘመን ነው (ኤር25፥1፤ 46፥2)።

1፥2 *ወሰዳቸው፤* ይሁዳ ከእግዚአብሔር ጋር የገባችውን ቃል ኪዳን ስላፈረሰች፣ ሰንበትን ስለሻረችና ጣዖትን ስላመለከች (ዘሌ25፥1-7፤26፥27-35፤2ዜና36፥14-21 ይመ) በናቡከደናፆር ተማርካ ወደ ባቢሎን ተወሰደች። የመጀመሪያው ምርኮ ዳንኤልን (በ605 ዓ.ቅ.ክ)፣ ሁለተኛው ምርኮ (597 ዓ.ቅ.ክ.) ሕዝቅኤልን ያቀፈ ነበር። በሦስተኛውም የምርኮ ጊዜ (586 ዓ.ቅ.ክ.) ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምንና በዚያ የነበረውን ቤተ መቅደስ አጠፉ።

1፥4 *የባቢሎናውያንን ቋንቋና ሥነ ጽሑፍ፤* ውስብስብ በሆነ በሱሜራውያንና በአካዲያን የኪዩኒፎርም ፊደል የተጻፈውን ጥንታዊ ሥነ ጽሑፍ የሚያጠቃልል ነው። ባቢሎን ብዙ ብሔረሰቦች የሚኖሩባት ስትሆን፣ የሕዝቧ መገናኛ ቋንቋም አራማይክ ነበር፤ የአራማይክ ቋንቋም በቀላሉ በሚለመድ ፊደል የሚጻፍ ነበር፤ (2፥4 ይመ)

1፥6 *ዳንኤል፤* "እግዚአብሔር ዳኛዬ ነው" የሚል ትርጕም አለው፤ አናንያ፤ "እግዚአብሔር ጸጋን ያሳያል" ማለት ነው። ሚሳኤል፤ "እንደ እግዚአብሔር ያለ ማን ነው?" ማለት ነው። *አዛርያ፤* "እግዚአብሔር ይረዳል" ማለት ነው።

1፥7 *ብልጣሶር፤* ምናልባት በባቢሎናውያን እምነት፣ "ቤል (ማርዱክ) ሕይወቱን ይጠብቃል" ማለት ነው። *ሲድራቅ* "የአኩ ትእዛዝ" ማለት ሊሆን ይችላል፤ አኩ የሱሜራውያን የጨረቃ አምላክ ነው። *ሚሳቅ፤* እንደ አኩ ያለ ማን ነው?" ማለት ሳይሆን አይቀርም። *አብደናጎ፤* "የኔጎ ወይም የኔቦ አገልጋይ" ማለት ነው።

1፥8 *በንጉሡ ምግብና የወይን ጠጅ፤* ምግብ መጀመሪያ ለጣዖት መሥዋዕት ሆኖ የሚቀርብ በመሆኑ፣ በናቡከደናፆር ገበታ ላይ ያለ ምግብ ሁሉ በእስራኤሎች ፊት የረከሰ ነበር። ከወይን ጠጁም በጣዖቱ መሠዊያ ላይ ይፈስ ነበር። በሥርዐታቸው መሠረት ንጹሕ ያልሆኑ እንስሳት ለመብል ከመቅረባቸው በተጨማሪ አስተራረዳቸውና አዘገጃጀታቸው ሕጉ በሚያዘው መሠረት አልነበረም። *ራሱን እንዳያረክስ...ፈቃድ ጠየቀው፤* እምነቱ የቱን ያህል ጽኑ እንደ ሆነ ገለጸ።

1፥9 *እግዚአብሔርም ለዳንኤል በጃንደረቦቹ አለቃ ፊት ሞገስን...ሰጠው፤* የዮሴፍና የዳንኤል የሥራ ኀላፊነት በብዙ መልክ ተመሳሳይነት ነበራቸው (ዘፍ39-41 ይመ)።

1፥12 *አገልጋዮችህን...ፈትነን፤* ዳንኤል ከዐመፅ ይልቅ አማራጭ የመፍትሔ ሐሳቦችን በማቅረብ አስተዋይነቱን ገለጸ። ዐሥር፤ ብዙውን ጊዜ ፍጹምነትን የሚያመለክት ቍጥር ነው።

*1፥17፤* ዳንኤልና ጓደኞቹ በእግዚአብሔር ርዳታ በኰከብ ቈጠራ ላይ የተመሠረተውን የባቢሎናውያንን ሥነ ጽሑፍና በሕልም አማካይነት የሚደረገውን የጥንቈላ አሠራር በሚገባ ዐወቁ። ነገር ግን ዐቢይ የሆነ ጕዳይ እንዲተረጕሙና እንዲተነብዩ (2፥3-11፤ 4፥7 ይመ) ባስፈለገ ጊዜ የአረማውያን ሥነ ጽሑፍ ዋጋ ቢስ ሆኖ ተገኘ። ዳንኤልም በትክክል ለመተርጐም የቻለው እግዚአብሔር ባደረገለት ልዩ መገለጥ ነበር (2፥17-28)።

1፥20 *አስማተኞች፤* የዘፍ 41፥8 ማብ ይመ። *ዐሥር፤*

እስራኤልም ከትውልድ አገሩ፣
ተማርኮ ይሄዳል::' "

## የጐመራ ፍሬ የሞላበት ቅርጫት

8 ጌታ እግዚአብሔር ይህን አሳየኝ፤ እነሆ፤ የጎመራ ፍሬ የሞላበት ቅርጫት ነበረ:: [2]እርሱም፣ "አሞጽ ሆይ፤ ምን ታያለህ?" አለኝ:: እኔም፣ "የጎመራ ፍሬ የሞላበት ቅርጫት አያለሁ" አልሁ:: ከዚያም በኋላ እግዚአብሔር እንዲህ አለኝ፤ "በሕዝቤ በእስራኤል ላይ ፍጻሜ መጥቶአል፤ ከእንግዲህም አልምራ ቸውም::"

[3]ጌታ እግዚአብሔር፣ "በዚያ ቀን የቤተ መቅደሱ ዝማሬ ወደ ዋይታ[a] ይለወጣል፤ እጅግ ብዙ የሆነ የሰው ሬሳ ወድቆ ይገኛል፤ ዝምታም ይሰፍናል" ይላል::

[4]እናንት ችግረኞችን የምትረግጡ፣
የምድሪቱንም ድኾች የምታጠፉ ይህን ስሙ፤

[5]እንዲህም ትላላችሁ፤
"መስፈሪያውን በማሳነስ፣
ዋጋውን ከፍ በማድረግ፣
በሐሰተኛ ሚዛን በማጭበርበር፣
እህል እንድንሸጥ፣
የወር መባቻ መቼ ያበቃል?
ስንዴም ለገበያ እንድናቀርብ፣
ሰንበት መቼ ያልፋል?"

[6]ድኻውን በብር፣
ችግረኛውንም በጥንድ ጫማ እንገዛለን፤
ግርዱን እንኳ በስንዴ ዋጋ እንሸጣለን::"

[7]እግዚአብሔር በያዕቆብ ክብር እንዲህ ሲል ምሎአል፤ "እነርሱ ያደረጉትን ሁሉ ከቶ አል ረሳም::

[8]"በዚህ ነገር ምድር አትናወጥምን?
በውስጧ የሚኖሩትስ ሁሉ አያለቅሱምን?

8፥1 አሞ7፥1
8፥2 ዘፍ40፥16፤ ኤር1፥13፤24፥3፤ ሰቆ4፥18፤ ሕዝ7፥2-9፤አሞ7፥8
8፥3 አሞ5፥16፤ 6፥10
8፥4 ኢዮ20፥19፤ መዝ14፥4፤ምሳ30፥14፤አሞ2፥7
8፥5 ዘፍ31፥7፤ ዘኍ10፥10፤ዘዳ25፥15፤2ነገ4፥23፤ነህ10፥31፤13፥15-16፤ ኢሳ58፥13 ሕዝ45፥10-12 ሆሴ12፥7፤ ሚክ6፥10-11፤ዘካ5፥6
8፥6 አሞ2፥6፤ 4፥1፤5፥11
8፥7 ኢዮ35፥15፤ መዝ47፥4፤ሆሴ8፥13
8፥8 ኢዮ9፥6፤ መዝ18፥7፤ኤር46፥8፤51፥29፤አሞ9፥5
8፥9 ኢዮ5፥14፤ ኢሳ59፥9-10፤ ኤር13፥16፤15፥9፤ ሕዝ32፥7፤ አሞ5፥8፤ሚክ3፥6፤ ማቴ27፥45፤ ማር15፥33፤ ሉቃ23፥44-45
8፥10 ዘፍ21፥16፤ ዘሌ13፥40፤ዘሌ26፥31፤ኢሳ3፥17፤ ኤር2፥19፤ሰቆ5፥15፤ ሕዝ7፥18፤ሆሴ2፥11፤ ኢል1፥8
8፥11 1ሳሙ3፥1፤ 2ዜና15፥3፤ኢሳ30፥20፤ ኤር30፥3፤31፥27
8፥12 ሕዝ20፥3:31
8፥13 ኢሳ9፥17፤ 41፥17፤ሆሴ2፥3
8፥14 1ነገ12፥29፤ መዝ46፥2፤አሞ5፥2:5፤ ሚክ1፥5

የምድር ሁሉመና እንደ ዐባይ ወንዝ ይነሣል፤
እንደ ግብፅ ወንዝም ወደ ላይ ይፈናጠራል፤
ተመልሶም ይወርዳል::"

[9]ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"በዚያ ቀን፣ ፀሓይ በቀትር እንድትጠልቅ
አደርጋለሁ፤
ምድርንም ደማቅ ብርሃን ሳለ በቀን
አጨልማታለሁ::

[10]ዓመት በዓላችሁን ወደ ልቅሶ፣
ዝማሬአችሁንም ሁሉ ወደ ዋይታ
እለውጣለሁ፤
ሁላችሁም ማቅ እንድትለብሱ፣
ጠጕራችሁንም እንድትላጩ አደርጋለሁ፤
ያን ጊዜ ለአንድያ ልጅ ሞት እንደሚለቀስበት፣
ፍጻሜውንም እንደ መራራ ቀን
አደርገዋለሁ::"

[11]ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"በምድር ላይ ረሐብን የምሰድበት ዘመን
ይመጣል፤
ይኸውም የእግዚአብሔርን ቃል
የመስማት ረሐብ እንጂ፣
እንጀራን የመራብ ወይም ውሃን
የመጠማት አይደለም::

[12]ሰዎች እግዚአብሔርን ለመሻት፣
ከባሕር ወደ ባሕር፣
ከሰሜን ወደ ምሥራቅ ይንከራተታሉ፤
ነገር ግን አያገኙትም::

[13]"በዚያ ቀን፣
"ቈነጃጅት ሴቶችና ብርቱዎች ጕልማሶች፣
ከውሃ ጥም የተነሣ ይዝላሉ::

[14]በሰማርያ ኀፍረት[b] የሚምሉ፣
ወይም፣ 'ዳን ሆይ፤ ሕያው አምላክህን'
የሚሉ፣

[a]3 *የቤተመቅደሱ ዘማሪያን ዋይታ ያሰማሉ የሚሉ አሉ::*
[b]14 *ወይም በአሼማ ወይም በማእት አማልክት::*

የግል ይዞታ የነበረው ርስት ተወስዶ ለሌሎች ተከፋፍሎ ይሰጣል ማለት ነው:: *በረከስ ምድር፤* ጣዖት የሚመለክበት ምድር የረከሰ በመሆኑ፣ በሥርዐቱ መሠረት ለክህነት አገልግሎት የነበረው ቅድስና ይረክሳል ማለት ነው (አማራጭ ትርጕሙን ይመ):: *እስ ራኤልም ከትውልድ አገሩ፤* አሞጽ ይህን ሐረግ (በዕብራይስጡ) ደጋግሞ ይጠቅሳል፤ ይኸውም፣ አሜስያስ ቀደም ብሎ በአጭሩ ከገለጸው የአሞጽ መልእክት የመጨረሻው ሁለት መሥመር ነው::

8፥1 *አሳየኝ፤* የ7፥1 ማብ ይመ::

8፥2 *የጐመራ ፍሬ ... ፍጻሜ መጥቶአል፤* በዕብራይስጥ ቋንቋ ሁለት ትርጕም ያለው ኅብር አገላለጽ ነው፤ እስራኤል የም ትነቀልበት ጊዜ እንደ ደረሰ ያመለክታል::

8፥3 *በዚያ ቀን፤* የ5፥18 ማብ ይመ:: *ዋይታ... ዝምታም፤* በዚህ የመከር ጊዜ የሚኖረው የምስጋና መዝሙር ሳይሆን፣ ከጭ ንቀት የተነሣ የሚሆን ጸጥታ ነው (ከዘሌ23፥39-41 ጋር ያነጻጽሩ)::

8፥5 *የወር መባቻ ... ሰንበት፤* የንግድ ሥራ የማይከሄድ ባቸው የሃይማኖት በዓላት ናቸው (ከዘኍ28፥9-15 ጋር ያነጻጽሩ):: *መስፈሪያውን በማሳነስ፣ ዋጋውን ከፍ በማድረግ፤* በሐሰተኛ ሚዛን ማለት ነው::

*8፥6፤* የ2፥6 ማብ ይመ ::

8፥7 *በያዕቆብ ክብር ...ምሎአል፤* እግዚአብሔር አምላኳ ስለ ሆነ እስራኤል በዚህ ትመካለች::

8፥8 *እንደ ዐባይ ወንዝ ይነሣል፤* በኢትዮጵያ ወቅቱን ጠብቆ ከሚዘንበው ከባድ ዝናም የተነሣ የዐባይ ወንዝ ግብፅ ሲደርስ በየዓመቱ እስከ ሃያ አምስት ጫማ ከፍ ይላል፤ ከፍ ብለው ከተ ሠሩት መንደሮችና ከተሞች በስተቀር ጉርፉ መሬውን ሸለቆ ያጥለቀልቃል፤ ውሃውም ለም የሆነ ብዙ ዐፈር ይዞ ይሄዳል::

8፥9 *በዚያ ቀን፤* የ5፥18 ማብ ይመ:: *ምድርንም... አጨልማታለሁ፤* በሌላ ስፍራ እንደተጠቀሰው፣ "የእግዚአብሔር ቀን" ፍጥረት እንዳልነበር እስኪ መስል ድረስ የተፈጥሮ ሥርዐት በመዛባቱና ብርሃን ወደ ጨለማ በመለወጡ ይታወቃል (ኢሳ13፥10፤ 24፥23፤34፥4፤50፥3፤ ሕዝ32፥7-8፤ ኢል2፥10:31፤ ሚክ3፥6 ይመ)

8፥10 *ልቅሶ* ንጉሥ ዳዊት እንዳደረገው ነው (2ሳሙ18፥33):: *ማቅ እንድትለብሱ፣ ጠጕራችሁንም እንድትላጩ፤* የሐዘን ምልክት ነው (ዘፍ37፥34፤ ኤር4፥5ይመ)፤ አንድያ ልጅ ለወደ ፊት የቤተ ሰቡ የኑሮ መሠረት ስለ ሆነ ተስፋ ተደርጎ የሚጠበቅ ልጅ ነው (ከ2ሳሙ18፥18 ጋር ያነጻጽሩ):: *መራራ ቀን* የክብረ በዓል ቀን ተቃራኒ ነው (አስ 9፥22)::

8፥11 *ዘመን* የእግዚአብሔር ፍርድ ተግባራዊ መሆን በሚጀምርበት ጊዜ ማለት ነው:: *የእግዚአብሔርን ቃል የመስ ማት ራብ፤* በታላቅ ጭንቅ ጊዜ እስራኤል ተስፋን የሚያመለክት የትንቢትን ቃል ለማግኘት ወደ እግዚአብሔር ዘወር ብላለች (ለም ሳሌ 2ነገ 19፥1-4:14፤22፥13-14፤ ኤር21፥2፤ ሕዝ14፥3:7 ይመ)፤ ይሁን እንጂ በሚመጣው የፍርድ ጊዜ እግዚአብሔር ለእንዲህ ዐይነቱ ጥያቄ መልስ የሚሰጠው በዝምታ ነው፤ ይህም አስፈሪ የእግዚ አብሔር ዝምታ ነው (1ሳሙ28፥6፤ ሕዝ7፥26፤20፥1-3፤ ሚክ3፥4:7 ይመ)::

8፥12 *ከባሕር ወደ ባሕር፣ ከሰሜን ወደ ምሥራቅ* በመላው የእስራኤል ምድርና በዮርዳኖስ ማዶ ያለውን ምድር ሳይቀር ለማለት ነው::

8፥13 *ጥም፤* ሥጋዊ ጥማት ብቻ ሳይሆን መንፈሳዊ ጥማትንም ሊያመለክት ይችላል:: ጕልበታቸው ተበልቶ አለቀ፤ ተወዳጆቹ ልጃገረዶችና ብርቱዎቹ ወንዶች ልጆች እንኳ ሳይቀሩ ዝለው ከጥቅም ውጭ ሆነዋል::

8፥14 *የሚምሉ፤* የሚምሉት በተለያዩ የማምለኪያ ስፍራ

ወይም 'ሕያው የቤርሳቤህ አምላክን[ጀ]'
ብለው የሚምሉ፣
ዳግመኛ ሳይነሡ፣ ለዘላለም ይወድቃሉ፡፡"

## እስራኤል ትጠፋለች

9 ጌታን በመሠዊያው አጠገብ ቆሞ አየሁት፤
እርሱም እንዲህ አለ፤
"መድረኮቹ እንዲናወጡ፣
ጕልላቶቹን ምታ፣
በሕዝቡም ሁሉ ራስ ላይ ሰባብራቸው፤
የቀሩትን በሰይፍ እገድላቸዋለሁ፤
ከእነርሱ አንድም ሰው አይሸሽም፤
ቢሸሽም የሚያመልጥ የለም፡፡
[2]መቃብር[ፐ] በጥልቀት ቈፍረው ቢወርዱም፣
እጄ ከዚያ ታወጣቸዋለች፤
ወደ ሰማይ ቢወጡም፣
ከዚያ አወርዳቸዋለሁ፡፡
[3]በቀርሜሎስ ጫፍ ላይ ቢሸሸጉም፣
አድኜ ፈልጌ ከዚያ አወርዳቸዋለሁ፤
እይዛቸዋለሁም፤
በጥልቅ ባሕር ውስጥ ከእኔ ቢሸሸጉም፣
በዚያ እባቡ እንዲነድፋቸው አዘዋለሁ፤
[4]በጠላቶቻቸው ተነድተው ለምርኮ ቢወሰዱም፣
በዚያ እንዲገድላቸው ሰይፍን
አዛለሁ፤
ለመልካም ሳይሆን ለክፉ፣
ዐይኔን በእነርሱ ላይ አደርጋለሁ፡፡
[5]ጌታ፣ እግዚአብሔር ጸባኦት፣
ምድርን ይዳስሳል፤
እርሷም ትቀልጣለች፤
በውስጥዋ የሚኖሩ ሁሉ ያለቅሳሉ፤
የምድር ሁለመና እንደ ዐባይ ወንዝ
ይነሣል፤
እንደ ግብፅ ወንዝም ይወርዳል፡፡
[6]መኖሪያውን[ጠ] በሰማይ የሚሠራ፣
መሠረቱንም[ጨ] በምድር የሚያደርግ፣
የባሕርን ውሃ የሚጠራ፣
በምድርም ገጽ ላይ የሚያፈስ፣
እርሱ ስሙ እግዚአብሔር ነው፡፡
[7]"እናንት እስራኤላውያን፣
ለእኔ እንደ ኢትዮጵያውያን
አይደላችሁምን?"
ይላል እግዚአብሔር
"እስራኤልን ከግብፅ፣
ፍልስጥኤማውያንን ከከፍቶር[ሰ]፣
ሶርያውያንንም ከቂር አላወጣሁምን?
[8]"እነሆ፤ የጌታ እግዚአብሔር ዐይኖች፣
በኀጢአተኛ መንግሥት ላይ ናቸው፤
ከምድር ገጽ፣ ፈጽሜ አጠፋዋለሁ፤
የያዕቆብን ቤት ግን፣
ሙሉ በሙሉ አልደመስስም፤"
ይላል እግዚአብሔር፡፡
[9]"እነሆ፤ ትእዛዝ እሰጣለሁ፤
እህል በወንፊት እንደሚነፋ፣
የእስራኤልን ቤት፣
በሕዝብ ሁሉ መካከል እንዲሁ አደርጋለሁ፤
ነገር ግን አንዲት ቅንጣት በምድር ላይ
አትወድቅም፡፡
[10]በሕዝቤ መካከል ያሉ፣
'ክፉ ነገር አያገኘንም ወይም አይደርስብንም'
የሚሉ፣
ኀጢአተኞች ሁሉ፣
በሰይፍ ይሞታሉ፡፡

9፥1 መዝ68፥21፤ ኤር11፥11
9፥2 ኢዮ7፥9፤ ኤር51፥53፤ ሕዝ26፥20፤ አብ1፥4
9፥3 ዘፍ49፥17፤ ኢዮ11፥20፤ መዝ68፥22፤139፥8-10፤ ኢሳ27፥1፤ ኤር16፥16-17፤ አሞ1፥2
9፥4 ዘሌ26፥33፤ ኤር21፥10፤39፥16፤ 44፥11፤ ሕዝ5፥12፤ 15፥7፥21 አሞ8፥8
9፥6 መዝ104፥1-3፥ 5-6፡13፤ ኤር43፥9፤ አሞ5፥8
9፥7 ዘፍ10፥14፤ ዘዳ2፥23፤2ነገ16፥9፤2 ዜና12፥3፤ ኢሳ20፥4፤ 22፥6፤43፥3፤ አሞ2፥10
9፥8 ኤር4፥27፤ 44፥27
9፥9 ኢሳ30፥28፤ ኤር31፥36፤ዳ39፥7፤ ሉቃ22፥31
9፥10 ኤር5፥12፤ 23፥17፤49፥37፤ ሕዝ20፥38፤ አሞ6፥3
9፥11 ዘፍ26፥22፤ መዝ53፥6፤80፥12፤ ኢሳ7፥2፤49፥8፤ ሕዝ17፥24፤ ሚክ7፥8፡11፤ዘካ12፥7 ፤14፥10

[ጀ]14 ወይም ኀይል [ፐ]2 ዕብራይስጡ ሲኦል ይለዋል፡፡ [ጠ]6 ዕብራይስጡ ለዚህ ሐረግ የሰጠው ትርጕም ምን እንደሆነ አይታወቅም፡፡ [ጨ]6 ዕብራይስጡ ለዚህ ሐረግ የሰጠው ትርጕም ምን እንደሆነ አይታወቅም፡፡ [ሰ]7 በላይኛው ዐባይ አካባቢ ያለ ሕዝብ ነው

ዎች ባሉት ሐሰተኛ አማልክት ነው (አማራጭ ትርጕሙን ይመ)፤ ሕዝቡ ከእግዚአብሔር ይልቅ በእነዚህ አማልክት ይታመኑ ነበር፡፡

9፥1 *ጌታን...አየሁት፤* የ7፥1 ማብ ይመ፡፡ በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር በምድር ላይ ቆሞ ነበር፡፡ *በመሠዊያው አጠገብ፤* ሕዝቡ የሰላምና የበረከት ቃል ለመስማት በሚጠብቁበት ስፍራ፣ እግዚአብሔር ጥፋትን ሊያመጣባቸው ተዘጋጅቶአል፡፡ *ጕልላቶቹን፤* በጌጣጌጥ ከተዋቡት ጕልላቶች ጀምሮ በታላላቅ ድንጋይ እስከ ታነጹት መድረኮች ድረስ እግዚአብሔር ቤተ መቅደሱን ሙሉ በሙሉ ያፈርሳል፡፡ የሚቀጥሉት ክፍሎች የሚደርሰውን ጥፋት ይገልጻሉ፡፡ በራእዩ ውስጥ እግዚአብሔር የሚታየው በኢየሩሳሌም ይሁን ወይም አይሁን ግልጽ አይደለም፤ ነገር ግን በቤቴል የቤተ መቅደስ ውቅር አለመኖሩን እናውቃለን፡፡

*9፥2-4፤* እነዚህ ጥቅሶች ሊፈጸም ካለው የእግዚአብሔር ፍርድ ማምለጥ እንደማይቻል ያመለክታሉ፡፡ አንድ ሰው ሊደርስበት የሚችለው ሐሳባዊ፣ "ጥልቀት" የሚያመለክት ሲሆን፣ በመዝ 139፥7-12 ላይ ከተጠቀሰው ጋር ሊነጻጸር ይችላል፡፡ የእግዚአብሔር ግዛት ሲኦልን ሳይቀር የሚያካትት ነው (ቍ2)፡፡

9፥3 *በቀርሜሎስ ጫፍ፤* የ1፥2 ማብ ይመ፡፡ *እባቡ፤* በጣዖት አምላኪዎች ተረታ ተረት መሠረት አስፈሪውን የባሕር አውሬ የሚያመለክት ነው፡፡ ሁሉም ነገር በእርሱ ቍጥጥር ሥር ስለ ሆነ ማንም ሰው ወደ ጥልቁ ሄዶ በመሸሸ ከእግዚአብሔር ሊያመልጥ አይችልም፡፡

9፥4 *በጠላቶቻቸው ተነድተው... አዛለሁ፤* በሕዝቦች መካከል ተበታትነው ያሉት እንኳ ከእግዚአብሔር ፍርድ አያመልጡም፡፡ *ለክፉ ዐይኔን በእነርሱ ላይ አደርጋለሁ፤* ከመዝ33፥18፤ 34፥15 ጋር ያነጻጽሩ፡፡

9፥5 *ጌታ፤* ፈጣሪ የሆነው የእስራኤል አምላክ፣ ፍጥረተ ዓለማትን ሁሉ ደግፎ የሚይዝና የሚጠብቅ መሆኑን የሚናገር ዝማሬአዊ አገላለጽ ሲሆን፤ ይህም የተጠቀሱትን የፍርድ ቃሎች በበለጠ የሚያጠናክር ነው (ከ4፥13፤5፥8-9 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡ *ምድርን... ትቀልጣለች፤* የመዝ46፥6 ማብ ይመ፡፡ *እንደ ዐባይ ወንዝ፤* 8፥8 እና ማብ ይመ፡፡

9፥6 *መኖሪያውን በሰማይ፤* ምድር ስትናወጥ የሚፈርሰውን የሰውን መለኪያ፣ ከእግዚአብሔር መለኪያ ጋር ያነጻጽራል (ቍ5)፡፡ መዝ104፥3 እና ማብውን ይመ፡፡ *የባሕርን፤* 5፥8 ማብ ይመ፡፡

9፥7 *ኢትዮጵያውያን፤* ከግብፅ በስተ ደቡብ የሚኖሩ (እና ከአማራጭ ትርጕሙ ጋር ያነጻጽሩ) ጠቈር ያለ ቆዳ ያላቸው ሕዝቦች ናቸው፡፡ *እስራኤልን... አላወጣሁምን?* የዘፀ20፥2 ማብ ይመ፡፡ እስራኤል ባለፉት ዘመናት እግዚአብሔር የሰጣት በረከት ወደፊት ለሚያደርግላት ቸርነት ዋስትና ሆኖአት በእርሱ ላይ መደገፍ አልቻለችም፡፡ በዕብሪት ላይ ከተመሠረተው ዐመፀኝነቷ የተነሣ እስራኤል በእርሱ ላይ ተስፋ ማድረግ አልቻለችም፡፡ የልቧ ትዕቢትና ዐመፀኝነት "በመውጣት" ዘመን ያገኘችው ልዩ ትርጕም እንዲወሰድባት አድርጉአል፤ ከግብፅ ወደ ከነዓን ያደረ ገችውም ጕዞ ሌሎች ሕዝቦች ካደረጉት ጕዞ የተለየ አልሆነም፡፡ *ፍልስጥኤማውያንን ከከፍቶር፤* የኤር 47፥4 ማብ ይመ፡፡ *ከቂር፤* የ1፥5 ማብ ይመ፡፡

9፥8 *በኀጢአተኛ መንግሥት፤* የተመረጠው ሕዝብ አለመታዘዝ ከሌሎች ሕዝቦች አለመታዘዝ ብሶ የተገኘውን እስራኤልን ማለት ነው (ከ1፥3-2፥16፤3፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡

9፥9 *በወንፊት፤* ስንዴው ከመሬት ታፍሶ በሚነፋበት ጊዜ አብሮት የሚሰበሰበውን ጥቃቅን ድንጋይና ሌላ የማያስፈልግ ነገር ሁሉ ያጠራል፡፡ *አንዲት ቅንጣት ...አትወድቅም፤* በወንፊት ሲነፋ እህሉ ብቻ ይቀራል፤ ሌላው ተጣርቶ ይጣላል፡፡

9፥10 *ኀጢአተኞች ሁሉ... ይሞታሉ፤* ይህም የሚሆነው በዐመፀኝነታቸው ስለ ጸኑ ነው፡፡

*9፥11፤* በአይሁድ ታልሙድ ይህ ጥቅስ ስለ መሲሑ እንደሚናገር ይታመናል፡፡ *አነሣዋለሁ፤* በአሞጽ የተነገረውን የፍርድ ቃል

### የእስራኤል መመለስ

[11] "በዚያ ቀን፣
የወደቀውን የዳዊትን ድንኳን አነሣለሁ፤
የተሰበረውን እጠግናለሁ፤
የፈረሰውን ዐድሳለሁ፤
ቀድሞ እንደነበረም አድርጌ እሠራዋለሁ፤
[12]ስለዚህ የኤዶምን ትሩፍ፣
በስሜ[ሀ] የተጠሩትንም ሕዝቦች ሁሉ
ይወርሳሉ፤"
ይላል ይህን የሚያደርግ እግዚአብሔር።

[13]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፤ ዐጫጁ ዐጭዶ ሳይጨርስ፣
ዐራሹ በላዩ የሚደርስበት፣
ችግኝ ተካዩም ገና ተክሎ ሳይጨርስ፣
ወይን ጨማቂው የሚደርስበት ጊዜ
ይመጣል፤
አዲስ የወይን ጠጅ ከተራሮች
ይንጠባጠባል፤
ከኰረብቶችም ሁሉ ይፈሳል።
[14]የተሰደደውን[ለ] ሕዝቤን እስራኤልን
እመልሳለሁ፤
እነርሱም የፈራረሱትን ከተሞች መልሰው
ሠርተው በውስጣቸው ይኖራሉ።
የወይን ተክል ተክለው፣ ጠጁን ይጠጣሉ፤
አትክልት ተክለው ፍሬውን ይበላሉ።
[15]እስራኤልን በገዛ ምድራቸው እተክላቸዋለሁ፤
ከሰጠኋቸውም ምድር፣ ዳግመኛ
አይነቀሉም"
ይላል አምላክህ እግዚአብሔር።

9፥12 ዘኍ24፥18፤ ኢሳ43፥7፤ ኤር25፥29፤ ሐዋ15፥16-17
9፥13 ዘሌ26፥5፤ መሳ9፥27፤ ሩት2፥3፤ ኤር31፥38፤33፥14፤ ኢል2፥24፤3፥18
9፥14 2ነገ19፥29፤ ኢሳ32፥18፤ 49፥8፤61፥14፤62፥9፤ ኤር29፥14፤30፥18፤31፥28፤33፥7፤ ሕዝ28፥25-26፤ 34፥13-14፤አሞ5፥11
9፥15 ዘፀ15፥17፤ ኢሳ60፥21፤65፥9፤ ኤር3፥18፤18፥9፤23፥8፤24፥6፤32፥15፤ ሕዝ28፥26፤ 34፥25-28፤37፥12፡35፤ኢል3፥20

[ሀ]12 *ዕብራይስጡ እንደ ሰብዓ ሊቃናቱ ትርጕም የሕዝቡ ትሩፋትንና ስሜን የሚጠሩ ሁሉ፣ እግዚአብሔርን ይፈልጋሉ።*
[ለ]14 *ወይም ዕጣ ፈንታቸውን አድሳለሁ እንደማለት ነው።*

*መሠረት* በማድረግ ተስፋን የሚያድስ ነው፤ ይህም ከዘፍ3፥15 ጀምሮ በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት የሚገኝ ቃል ነው፤ ይኸውም ከፍርድ በኋላ እግዚአብሔር በረከትን እንደሚያመጣና እስራኤልንም ፈጽሞ እንደማይተው ያመለክታል። *ድንኳን፤* በቀሙ፣ "ጎጆ" ማለት ሲሆን የዳዊትን ሥርወ መንግሥት ወይም የዐሥራ ሁለቱ ነገዶች ጥምር መንግሥት የሆነውን የዳዊትን መንግሥት ሊያመለክት ይችላል። "ጐጆ" የሚለው ቃል የተመረጠው የዳዊትን ከዝቅተኛ ቦታ መነሣት ለማስታወስ ይሆናል። *እንደነበረም፤* በዳዊትና በሰሎሞን ጊዜ እንደ ነበረው ለማለት ነው።

9፥12 *የኤዶምን ትሩፍ፤* እስራኤል ከተቀጣች በኋላ ከጨካኝ ጠላቶቿ የተረፈውን ሁሉ ለማለት ነው (የ1፥11 ማብ ይመ)። *በስሜ የተጠሩትንም ሕዝቦች ሁሉ፤* ዳዊት በእስራኤል ዙሪያ የነበሩትን ሁሉ እንደ ገዛ በማስታወስ፣ እግዚአብሔር የቀባው የወደ ፊቱ ንጉሥ የሚያስተዳድረው ግዛት ዳር ድንበር ከየት እስከ የት እንደሚዘልቅ የሚያመለክት ነው። ይህም ለአብርሃምና ለዳዊት የተደረጉ ኪዳኖች መፈጸማቸውን ያመለክታል። መሲሑ በኤዶም የተመሰሉትን የቀድሞ ጠላቶችን እንኳ ጨምሮ ይገዛል (የኢሳ34፥5 ማብ ይመ)። *ይህን የሚያደርግ፤* የተናገረውን የሚያደርግ እግዚአብሔር ነው።

*9፥13-15፤* ጥፋት፣ እጦትና ሞት እንደሚሆን ከተነበየ በኋላ (ከ5፥9፡11፡27 ጋር ያነጻጽሩ) የመጨረሻ ቃሉ ወቅቱ በመፈራረቅ መዝራትና ማጨድ የማይቋረጡበትንና አዲስ ምርት የሚታይበትን የከበረውን የገነትን ሕይወት በሥዕላዊ መልክ አቀረበ። ይህም በ4፥6-11 ከላይ ከተገለጸው ጋር የሚቃረን ነው።

*9፥13፤* ከኢል 3፥18 ጋር እንደሚመሳሰል ያስተውሉ።

9፥14-15፤*እመልሳለሁ ... ሠርተው ... ተክለው፤* በተስፋ ዩቱ ምድር እግዚአብሔር ሕዝቡን አምራች፣ ፍሬያማና ሰላማቸው የተጠበቀ ያደርጋቸዋል።

9፥14፤ *ሕዝቤን፤* የ7፥8 ማብ ይመ፤ ከሆሴ 1፥9 እንዲሁም ከሆሴ2፥23 ጋር ያነጻጽሩ። የፈራረሱትንም ከተሞች መልሰው ይሠራሉ፤ ኢሳ58፥12 እና ማብ ይመ።

9፥15 *ዳግመኛ፤* እስራኤል ለመጨረሻ ጊዜ ተመልሳ ሙሉ በሙሉ ከተገነባች በኋላ ዳግም አትደመሰስም። *አምላክህ* ከሆሴ1፥9 እንዲሁም ከሆሴ 2፥23 ጋር ያነጻጽሩ።

# ትንቢተ አብድዩ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ይህን መጽሐፍ የጻፈው አብድዩ ሲሆን፣ የስሙ ትርጕም "የእግዚአብሔር አገልጋይ" ማለት ነው:: "አብድዩ" የሚለው ስም በዚያን ጊዜ የተለመደ ስም ነበር (1ነገ 18፥3-16፤ 1ዜና 3፥21፤ 7፥3፤ 8፥38፤ 9፥16፤ 12፥9፤ 27፥19፤ 2ዜና 17፥7፤ 34፥12፤ ዕዝ8፥9፤ ነህ10፥5፤ 12፥25 ይመ):: የአባቱም ስም ሆነ የትውልድ ቦታው የት እንደ ሆነ አልተገለጸም::

### የተጻፈበት ጊዜና ቦታ

የተጻፈበትን ጊዜና ቦታ ለይቶ የማወቁ ጕዳይ አከራካሪ (አነጋጋሪ) ነው:: ትንቢቱ የተጻፈበትን ጊዜ ለማወቅ በቍ11-14 ላይ የተጻፈውን ሐሳብ፣ በእስራኤል ታሪክ ውስጥ ጕልሕ ስፍራ ካላቸው ቀጥሎ ከተጠቀሱት ሁለት ድርጊቶች ከአንዱ ጋር ማገናዘብ ያስፈልጋል::

1. በኢዮራም ዘመነ መንግሥት ፍልስጥኤማውያንና ዐረቦች በኢየሩሳሌም ላይ ያደረጉት ወረራ (853-841 ዓ.ቅ.ክ.)፤ 2ነገ 8፥20-22፤2ዜና21፥8-20 ይመ:: ከዚህ አንጻር ሲታይ አብድዩ ኤልሳዕ በነበረበት ዘመን ነበር ማለት ነው::
2. ባቢሎናውያን በኢየሩሳሌም ላይ ያደረጉት ወረራ (605-586 ዓ.ቅ.ክ)፤ ይህ ከሆነ አብድዩ ኤርምያስ በነበረበት ዘመን ነበረ:: ይኸኛው አማራጭ የበለጠ አሳማኝ ይመስላል:: በአብ ከቍ1-9 እና በኤር49፥7-22 መካከል ያለው መመሳሰል፣ ብዙ ሰዎች በአብድዩና በኤርምያስ መጽሐፍ መካከል አንድ ዐይነት መደጋገፍ አለ ብለው ለመናገር ምክንያት ሆኖአቸዋል፤ ሆኖም ሁለቱም ነቢያት ለኛ ካልታወቀ ከአንድ የጋራ ምንጭ በመቅዳት ጽፈውም ሊሆን ይችላል::

### የመጽሐፉ ወጥነትና መሪ ሐሳቡ

የዚህን አጭር ትንቢት ወጥነት በሚመለከት እንድንጠራጠር የሚያደርገን የጐላ ምክንያት የለም:: የመጽሐፉ መሪ ሐሳብ፣ በነበራት ጸጥታና ሰላም የታበየችው ኤዶም እስራኤል በባዕዳን ኀይል በመ ጥፋቷ ደስ መሰኘቷን የሚያመለክት ነው:: ስለዚህ ኤዶም በዚህ ሁኔታ በእስራኤል መጥፋት ተባባሪ በመሆንዋ፣ የእግዚአብሔር ቍጣ በላይዋ ይመጣል፤ እርሷ ራሷ ትጠፋለች፤ ነገር ግን የጽዮን ተራራና እስራኤል ከጥፋት ይድናሉ፤ የእግዚአብሔርም መንግሥት ድል ያደርጋል::

ኤዶም በእስራኤል ላይ የፈጸመችው የጠላትነት ድርጊት የእስራኤልን ዕድሜ አራዝሞታል:: በእስራኤልና በኤዶም መካከል ያለውን ግንኙነት ለመገንዘብ ቀጥሎ የተጠቀሱትን የመጽሐፍ ቅዱስ መረጃዎች መመልከቱ ጠቃሚ ነው:: ዘፍ27፥41-45፤ 32፥1-21፡33፡36፤ ዘፀ15፥15፤ ዘኍ20፥14-21፤ ዘዳ2፥1-6፤23፥7፤ 1ሳሙ22ን ከመዝ52ጋር፤ 2ሳሙ8፥13-14፤ 2ነገ8፥20-22፤ 14፥7፤ መዝ83፤ ሕዝ35፤ ኢዮ3፥18-19፤ አሞ1፥1-12፤ 9፥1::)

ኤዶማውያን ከእስራኤላውያን ጋር የተዛመዱ ስለሆኑ (ቍ10) በጠላትነት መቆማቸው በእጅጉ የሚያስ ወቅሣቸው ነው:: ኤዶም እስራኤልን ለመርዳት ወደ ኋላ ማለትዋና ያሳየችው ግልጽ ተቃውሞ ሙሉ በሙሉ የሚያስጠይቃት ነው:: እግዚአብሔር ዔሳውን (መጥላቱ) (ዘፍ 25፥23፤ ሚል1፥3፤ ሮሜ9፥13) በምንም መንገድ ኤዶማውያንን ነጻ ሊያደርጋቸው አይችልም:: ኤዶም በተራራ ላይ ባሉት ምሽጎችዋ የተመካች ቢሆንም፣ ከዚያ ትወርዳለች፤ ትበዘበዛለችም:: እስራኤል ግን እግዚአብሔር ከእርስዋ ጋር በመሆኑ ብልጽግናዋ ይበዛል::

### አስተዋፅኦ

1 ርእስና መግቢያ (1)

2 በኤዶም ላይ የተነገረ ፍርድ (2-14)

- ሀ. ኤዶም እንደምትጠፋ መገለጹ (2-7)
  1. መዋረዷ (2-4)
  2. ፍጹም መደምሰሷ (5-7)
- ለ. የኤዶም መጥፋት እርግጠኛነት (8-14)
  1. ኀፍረቷና ጥፋቷ (8-10)
  2. በእስራኤል ላይ የፈጸመችው በደል (11-14)

3 የጌታ ቀን (15-21)

- ሀ. ፍርድ በአሕዛብ ላይ፣ ትድግና ግን ለጽዮን (15-18)
- ለ. የእግዚአብሔር መንግሥት መመሥረት (19-21)

## የአብድዩ ራእይ፤

[1]ጌታ እግዚአብሔር ስለ ኤዶም እንዲህ
ይላል፤
*ከእግዚአብሔር* ዘንድ መልእክት ሰምተናል፤
መልእክተኛውም ወደ አሕዛብ ተልኮ እንዲህ
ብሎአል፤
"ተነሡ፤ እርሷን ለመውጋት እንውጣ።"
[2]"እነሆ፤ በአሕዛብ መካከል ታናሽ አደርግሃለሁ፤
እጅግ የተናቅህ ትሆናለህ።
[3]አንተ በሰንጣቃ[ሀ] ዐለት ውስጥ የምትኖር፣
መኖሪያህንም በከፍታ ስፍራ ያደረግህ፣
ለራስህም፣
'ማን ወደ ምድር ሊያወርደኝ ይችላል?' የምትል፣
የልብህ ትዕቢት አታልሎሃል።
[4]እንደ ንስር መጥቀህ ወደ ላይ ብትወጣ፣
ጐጆህንም በከዋክብት መካከል ብታደርግ፣
ከዚያ አወርድሃለሁ"
ይላል እግዚአብሔር።
[5]"ሌቦች ወደ አንተ ቢመጡ፣
ዘራፊዎችም በሌሊት ቢገቡ፣
የሚሰርቁት የሚፈልጉትን ያህል
ብቻ አይደለምን?
ወይን ለቃሚዎች ወደ አንተ ቢመጡ፣
ጥቂት ቃርሚያ አይተዉምን?
አንተ ግን ምንኛ ጥፋት ይጠብቅሃል!
[6]ዔሳው ግን እንዴት ተዘረፈ?
የሸሸገውስ ሀብት ምንኛ ተመዘበረ!
[7]ወዳጆችህ ሁሉ ወደ ድንበር ይገፉሃል፤
ጓደኞችህ ያታልሉሃል፤ ያሸንፉህማል፤
እንጀራህን የበሉ ወጥመድ ይዘረጉብሃል፤[ለ]
አንተ ግን አታውቀውም።
[8]"በዚያ ቀን ጥበበኛ ሰዎችን ከኤዶም፣
አስተዋዮችንም ከዔሳው ተራሮች አልደመ
ስስምን?"
ይላል እግዚአብሔር ።
[9]ቴማን ሆይ፤ ተዋጊዎችህ ይደነግጣሉ፤
በዔሳውም ተራሮች ያለ ሁሉ፣
ተገድሎ ይጠፋል።
[10]በወንድምህ በያዕቆብ ላይ ስላደረግኸው ግፍ፣
በዕፍረት ትሸፈናለህ፤
ለዘላለምም ትጠፋለህ።
[11]እንግዶች ሀብቱን ዘርፈው ሲሄዱ፣
ባዕዳንም በበሮቹ ሲገቡ፣
በኢየሩሳሌምም ላይ ዕጣ ሲጣጣሉ፣
በዚያ ቀን ገለልተኛ ሆነህ ተመለከትህ፣
አንተም ከእነርሱ እንደ አንዱ ሆንህ።
[12]ክፉ ቀን በገጠመው ጊዜ፤
በወንድምህ ሥቃይ መደሰት አልነበረብህም፤
በጥፋታቸው ቀን፣ የይሁዳ ሕዝብ ሲያዝኑ
ሐሤት ማድረግ አልነበረብህም፤
በጭንቀታቸውም ቀን፣
በትዕቢት ልትናገር አይገባህም ነበር።
[13]በጥፋታቸው ቀን፣
በሕዝቤ በር መግባት የለብህም ነበር፤
በጥፋታቸው ቀን፣
በጭንቀታቸው መደሰት አልነበረብህም፤
በጥፋታቸው ቀን፣
ሀብታቸውን መዝረፍ አይገባህም ነበር።
[14]ስደተኞቻቸውን ለመግደል፣

[ሀ]3 ወይም *በሴላ*
[ለ]7 የዚህ ሐረግ የዕብራይስጡ ትርጓሜ በእርግጠኝነት አይታወቅም።

1፥1 ዘፍ25፥14፤ ኢሳ1፥1፤11፥14፤ 18፥2፤34፥11፤ 63፥1-6፤ኤር6፥4-5፤ 49፥7-22፤ሕዝ25፥12-14፤32፥29፤ አሞ1፥11-12
1፥2 ዘኍ24፥18
1፥3 2ዜና25፥11-12፤ኢሳ16፥1፡6
1፥4 ኢዮ20፥6፤ ኢሳ10፥14፤14፥13
1፥5 ዘዳ4፥27፤ 24፥21፤ኢሳ24፥13
1፥7 መዝ41፥9፤ ኤር30፥14
1፥8 ኢዮ5፥12፤ ኢሳ29፥14
1፥9 ዘፍ36፥11፡34
1፥10 መዝ137፥7፤ ሕዝ25፥12-14፤35፥9፤ ኢል3፥19፤ አሞ1፥11-12
1፥11 ኢዮ6፥27፤ ሕዝ24፥6፤አሞ1፥6
1፥12 ኢዮ31፥29፤ መዝ137፥7፤ ምሳ17፥5፤24፥17፤ ሕዝ25፥6፤35፥15፤ ሚክ4፥11፤7፥8
1፥13 ሕዝ35፥5
1፥14 1ነገ18፥4

1፤ *ራእይ*፤ በብሉይ ኪዳን ከእግዚአብሔር የሆነውን መገለጥ ለማመልከት አገልግሎት ላይ የዋለ አገላለጽ ነው። *አብድዩ*፤ በመግቢያው ላይ "ጸሓፊ" የሚለውን ይመ። *ሰምተናል (እኛ)*፤ የሚለው ቃል (1) በአርታኢነት ጽሑፉን ያዘጋጁትን ወይም (2) ነቢዩ ራሱን ከእስራኤል ሕዝብ ጋር አንድ አድርጎ በመቍጠር የተናገረውን ወይም (3) ሌሎች ነቢያት በኤዶም ላይ የተናገሩት የፍርድ ቃል ሊሆን ይችላል። በዚህም ሆነ በዚያ የሚቀጥሉት ጥቅሶች በቍ2 ለሚጀምረው ለአብድዩ ትንቢታዊ መልእክት መድረክ አመቻችተዋል። *መልእክት*፤ ወይም ዜና ማለት ነው። ኤዶምን ለመውጋት እንዲነሡ ጥሪ ያደርግ ዘንድ መልእክተኛ ወደ አሕዛብ ተልኮአል፤ የተላከውም በአንዳንድ የኤዶም ተባባሪዎች መካከል ሤራ በመካሄዱ ሳይሆን አይቀርም (ቍ7 ይመ)። ኤዶም ተራሮች ላይ ባሉ ምሽጎችዋና ጠቢብ በሆኑ ሰዎችዋ ብትታመንም (ቍ2-4፡8-9)፣ የእስራኤል ጠላት ስለሆነች አብድዩ የእግዚአብሔርን ፍርድ በእርሷ ላይ ዐውጆአል።

2፤ *ታናሽ አደርግሃለሁ*፤ "ቈራርጬሃለሁ" ከሚለው የመደበኛ ቋንቋ ካልሆነ አነጋገር ጋር ይህን ያነጻጽሩ።

3፤ *በዐለት*፤ አማራጭ ትርጕሙን ይመ። ሴላ የኤዶም ዋና ከተማ ነበረች። ምናልባት በኋላ ፔትራ የተባለችው ድንጋያማ ስፍራ ስትሆን ከሙት ባሕር በስተደቡብ ጫፍ ሰማንያ ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ ትገኛለች። የሴላም ሆነ የፔትራ ትርጕም "ዐለት" ወይም "ቀጥ ያለ ገደል" ማለት ነው፤ የ2ነገ 14፥7 ማብ ይመ።

4፤ *ንስር*፤ ኩሩና የተዋበ ወፍ ሲሆን፣ በብርታት፣ ሩቅ ያለውን በማየትና በፈጣንም በራሪነቱ የሚታወቅ ነው። *በከዋክብት*፤ የማይደረስባቸውን ታላላቅ ተራሮችን ለማመልከት የገባ ግነታዊ አገላለጽ ነው።

5፤ *ሌቦች...ወይን ለቃሚዎች*፤ በኤዶም ላይ የተነገረውን ተመሳሳይ ንግር በኤር 49፥9 ይመ።

6፤ *የሸሸገውስ ሀብት*፤ ዳዮዶረስ ሲኩለስ የተባለ የጥንት ግሪክ ጸሓፊ፣ ኤዶማውያን በንግድ ያከማቹትን ሀብት ከዐለት በተሠራ ጋን ውስጥ ያስቀምጡ እንደነበረ ጽፎአል።

7፤ *ወጥመድ ይዘረጉብሃል*፤ በዕብራይስጡ ይህ አባባል፣ በሚተማመኑ የቅርብ ወዳጆች መካከል የተፈጠረውን ክሕደት ያመለክታል፤ አማራጭ ትርጕሙን ይመ ፤ በአንድ ማእድ አብረው የበሉ ሁሉ ወዳጆች ናቸው፤ (የመዝ41፥9 ማብ ይመ)።

8፤ *በዚያ ቀን*፤ ኤዶም የምትጠፋበት ቀን ማለት ነው፤ ይሁን እንጂ ቃሉቹ የሥነ ፍጻሜን ሐሳብ ያንጸባርቃሉ፤ በብሉይ ኪዳን የትንቢት ቃል የኤዶም ስም ሲጠቀስ፣ እግዚአብሔርንና የእርሱን መንግሥት የሚቃወሙትን የዓለም ኀይላት ይወክላል፤ በእርሷ ላይ የተላለፈው ፍርድ ከወዲሁ የሚያመለክተው፣ እግዚ አብሔር በዚያው ቀን እንዲህ ያሉ ተቃዋሚዎችን ሁሉ ፈጽሞ እንደሚደመስስ ነው። *ጥበበኛ ሰዎችን*፤ ኤዶም ለሰላሟና ለደህንነቷ የተመካችባቸውን የሚያመለክት ነው (ኤር49፥7 ይመ)። ከኢዮብ ባልንጀሮች አንዱ የነበረው ኤልፋዝ ቴማናዊ ነው። ቀጥሎ ያለውን ማብ ይመ። *ከዔሳው*፤ የኤዶም ሌላ ስሙ ነው (ዘፍ36፥1 ይመ)።

9፤ *ቴማን*፤ በኤር 49፥7፡20 እንዳለው መላው ኤዶምን የሚያመ ለክት ነው (አሞ1፥12 ይመ)። "ቴማን" ማለት ደቡብ ማለት ሲሆን ስሙ ኤዶም በደቡብ በኩል ያለ ምድር መሆኑን ሊያመ ለክት ይችላል፤ ይሁን እንጂ አንዳንዶች ቴማንን ከፔትራ በስተ ምሥራቅ ከአራት እስከ አምስት ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ ከምት ገኘው ታዊላን ጋር ያመሳስላሉ።

10፤ *በወንድምህ በያዕቆብ*፤ የኤዶም ወንጀል ከባድና የማ ይታለፍ ነው፤ ምክንያቱም የተፈጸመው በደል ወንድም በሆነ ሕዝብ ላይ ነበር። *በዕፍረት ትሸፈናለህ*፤ ብዙውን ጊዜ ዕፍረት ከዕራቍትነት ጋር የተያያዘ ስለሆነ፣ አስገራሚ አገላለጽ ነው። በመግ ቢያው ላይ "የተጻፈበት ዘመንና ቦታ" የሚለውን ይመ።

11፤ *እንግዶች...ባዕዳንም*፤ እነዚህ ቃላት የኤዶምን ኀጢ አት አጕልተው የሚያሳዩ ናቸው፤ የወንድምን ተግባር ሳይሆን (ቍ12) የባዕድን ሥራ ፈጽሞአልና።

*12-14*፤ በኤዶም ክፋት ላይ የተጠቀሰ የግሣጼ ቃል ነው። በዚህ ክፍል የተጠቀሱት ስምንት የተግሣጽ ቃሎች ከአጠቃላዩ ተነሥተው ወደ ተወሰነው ወደ አንዱ የመጡ ናቸው። ይሁዳ

በመንታ መንገድ መጠባበቅ አይገባህም ነበር፣
በጭንቀታቸው ቀን፣
የተረፉትን አሳልፈህ መስጠት አልነበረብህም።
[15]"በአሕዛብ ሁሉ ላይ፣
የእግዚአብሔር ቀን ደርሶአል፤
አንተ እንዳደረግኸው፣ በአንተም ላይ ይደረጋል፤
ክፉ ሥራህም በራስህ ላይ ይመለሳል።
[16]እናንተ በቅዱሱ ተራራዬ እንደ ጠጣችሁ፣
አሕዛብ ሁሉ ዘወትር ይጠጣሉ፤
ይጠጣሉ፤ አብዝተውም ይጠጣሉ፤
ከዚህም በፊት እንዳልሆኑት ይሆናሉ።
[17]ነገር ግን በጽዮን ተራራ ነጻ መውጣት ይሆናል፤
የያዕቆብ ቤትም እርሷ የተቀደሰች ትሆናለች፤
ርስታቸውን ይወርሳሉ።
[18]የያዕቆብ ቤት እሳት፣
የዮሴፍም ቤት ነበልባል ይሆናል፤
የዔሳው ቤት ገለባ ይሆናል፤
ያቃጥሉታል፤ ይበሉትማል፤
ከዔሳው ቤት የሚተርፍ፣ አይኖርም።"
እግዚአብሔር ተናግሮአል።
[19]የኔጌብ ሰዎች፣
የዔሳውን ተራራ ይይዛሉ፤
ከተራራው ግርጌ ያሉ ሰዎችም፣
የፍልስጥኤማውያንን ምድር ይወርሳሉ፤
የኤፍሬምንና የሰማርያንም ዕርሻ ይይዛሉ፤
ብንያምም ገለዓድን ይወርሳል።
[20]በከነዓን ያለው ይህ የእስራኤል ስደተኞች ወገን፣
እስከ ሰራጵታ ያለውን ምድር ይወርሳል፤
በሰፋራድም ያሉ የኢየሩሳሌም ስደተኞች፣
የኔጌብን ከተሞች ይወርሳሉ።
[21]የዔሳውን ተራሮች ለመግዛት፣
ነጻ አውጪዎች ወደ ጽዮን ተራራ ይወጣሉ፤
መንግሥቱም የእግዚአብሔር ይሆናል።

1፥15 ኤር46፥10፤ 50፥29፤ ሕዝ30፥3፤ ኢል2፥31፤ አሞ5፥18፤ዕን2፥8
1፥16 ዘፀ15፥17፤ ኢሳ51፥17፤ ኤር25፥15፤ 49፥12፤ሰቆ4፥21-22፤ ሕዝ25፥12-14
1፥17 መዝ69፥35፤74፥2፤ ኢሳ4፥3፤14፥12፤ ኢል2፥32፤ አሞ9፥11-15፤ ዘካ8፥12
1፥18 ኢሳ1፥31፤ ኤር49፥10፤ ዘካ12፥6
1፥19 ዘኍ1፥36፤ ኢሳ11፥14፤ኤር31፥5
1፥20 1ነገ17፥9-10 ፤ኤር33፥13 ፤ሉቃ4፥26 ራእ11፥15
1፥21 ዘዳ28፥29፤መሳ3፥9፤መዝ22፥28፤47፥9፤66፥4፤ዳን2፥44፤ ዘካ14፥9:16፤ሚል1፥14፤

ክፉ ዕጣ በገጠመው ጊዜ ኤዶም ያሳያውን ሁኔታ ለመረዳት ሕዝ 35፥13 እና መዝ137 ይመ።

15፤ *በአሕዛብ ሁሉ ላይ የእግዚአብሔር ቀን ደርሷል፤* "በዚያ ቀን" (ቍ8)፣ በሚለው ሐረግ ውስጥ ሥነ ፍጻሜን የሚያመለክት ጭላንጭል ካለ፣ እዚህ ላይ ብርቱ የጨረርን ብርሃን ያመለክታል፤ የእግዚአብሔርን ቀን ፍርድን በኤዶም ላይ ብቻ ሳይሆን ኤዶምንም ጨምሮ ፍርድን በአሕዛብ ላይ ሲያመጣ ድነትን ግን ለያዕቆብ ቤት ያመጣል። *በራስህ ላይ፤* ኤዶም በእግዚአብሔር ሕዝብ ላይ ለፈጸመችው ክፉት በምላሹ የአጸፋ ቅጣት እንደሚያገኛት ከቍ 11-14 በዝርዝር ተጽፎአል። ሕዝቅኤል በም35 ላይ ኤዶምን ማውገዙ ለሚፈጸመው ማንኛውም በደል ተመሳሳይ ቅጣት እንደሚሰጥ ያመለክታል።

16፤ *እንደጠጣችሁ፤* ኤዶማውያን ቅዱሱን ተራራ በስካርና በፈንጠዝያ እንዳረከሱት ሁሉ አሕዛብም እንዲሁ ይጠጣሉ፤ ደግሞም ይጠጣሉ። ይሁን እንጂ የሚጠጡት መራራውን የእግዚአብሔር ፍርድ ነው፤ ይህንንም ያለማቋረጥ እንዲጠጡት ይደረጋል። በቅጣት ስለ መጠጣታቸው የሚያመለክተውን ኤር25፥15-16፤49፥12 ይመ።

17፤ *ነገር ግን በጽዮን ተራራ ነጻ መውጣት ይሆናል፤* ከዚህ ጥቅስ ጀምሮ በያዕቆብ ቤት ያለው በረከት ተጠቅሶአል። ሥነ ፍጻሜን የሚያመለክቱ ጥቅሶች ጣምራ ፍች አላቸው፤ በእግዚአብሔር ጠላቶች ፍርድን ለእግዚአብሔር ሕዝብ ግን በረከትን ያመለክታሉ።

18፤ *የያዕቆብ ... የዮሴፍም፤* ቀደም ብሎ እግዚአብሔር ሌሎችን አሕዛብ ተጠቅሞ፣ኤዶምን እንደሚያጠፋ ተጠቅሶአል፤ ቍ7፤ አሁን ግን በእግዚአብሔር ሕዝብ እንደሚፈጸም ተገልጾአል። *የሚተርፍ አይኖርም፤* ለዔሳው የተነገረው የመጨረሻው ቃል፣ የእርሱ ሕዝብ ወይም ቤቱ ፈጽሞ እንደሚጠፋ ነው፤ ስለዚህ የሚተርፍ ኤዶማዊ አይኖርም ማለት ነው፤ ሆኖም አሞ 9፥12ን ከሐዋ15፥17 ጋር ያነጻጽሩ፤ የአሞ 9፥12 ማብ ይመ።

19፤ *ሰዎችም...ይይዛሉ፤* ኤዶም ሙሉ በሙሉ ከተደመሰሰ በኋላ ሌሎች የኤዶምን ግዛት ይይዛሉ፤ እነማን እንደሆኑ ግልጽ በሆነ መንገድ ባይጠቀስም፣ በሚቀጥሉት ጥቅሶች እንደሚታየው የእስራኤል ቅሬታዎች ሊሆኑ እንደሚችሉ ነው። *ኔጌብ፤* የዘፍ12፥9 ማብ ይመ። *የፍልስጥኤማውያን፤* የዘፍ10፥14ማብ ይመ: *ገለዓድ፤* የዘፍ31፥21፤ የማሕ4፥1 ማብ ይመ።

20፤ *ሰራጵታ፤* የ1ነገ17፥9 ማብ ይመ። *ሰፋራድ፤* በትንሹ እስያ ያለችው ሳርዲስ የዛሬዪቱን ቱርክ ያመለክታል ተብሎ የሚታመን ሲሆን አንዳንዶች ደግሞ የግሪክን ከተማ እስፓርታን ሊያመለክት ይችላል ይላሉ።

21፤ *ነጻ አውጪዎች፤* ነቢዩ እስካሁን በጽዮን ዙሪያ ያለውን መሬት ስለመያዝ ሲያትት ቆይቶ፣ አሁን ደግሞ ማእከል ወደ ሆነው ነገር ዘወር አለ። "ነጻ አውጪዎቹ" ከጽዮን ተራራ ወጥተው የዔሳውን ተራሮች ይገዛሉ። የጽዮን ተራራ ከዔሳው ተራሮች ላቅ ብሎ ክቡር ሆኖአል። አቻ የሌለው መሲሕ በመጨረሻ በአሻጋሪ እንዲታይ ሆኖአል። *መንግሥቱም የእግዚአብሔር ይሆናል፤* የትንቢቱ መደምደሚያና የታሪክ ፍጻሜ ነው። የመጽሐፍ ቅዱስም የመጨረሻው መጽሐፍ ይህንኑ ሐሳብ ያስተጋባል (ራእ11፥15)።

# ትንቢተ ዮናስ

## መግቢያ

### አሰያየሙ

መጽሐፉ የሚጠራው በዋናው ገጸ ባሕርይ በዮናስ ስም ሲሆን፣ የስሙም ትርጒም "ርግብ" ማለት ነው:: የስሜኑ መንግሥት "አእምሮ የሌለውና በቀላሉ የሚታለል" መሆኑን ለማመልከት ኤፍሬምን እንደተነጻጸረ ዘይቤ የተጠቀመበትን ከሆሴ 7፥11 ላይ ይመ:: በተጨማሪ መዝ 68፥13፤ 74፥19 እና ማግብ ይመ::

### ጸሐፊው

ጸሐፊው ማን እንደ ሆነ በመጽሐፉ ውስጥ የተገለጸ ነገር ባይኖርም፣ በታሪክ ግን ነቢዩ ራሱ ማለትም በዛብሉን (ኢሱ 19፥10:13) በምትገኘው ጋትሔፌር (2ነገ 14፥25)የሚኖረው የአማቴ ልጅ (1፥1) ዮናስ እንደጻፈው ይነገራል:: ኤልያስንና ኤልሣዕን በሚመለከት ከተጻፈው ጽሑፍ ጋር ሲነጻጸር ብዙ የሚመሳሰልበት ሁኔታ ስለሚታይ፣ ስለ እነዚህ ነቢያት የጻፈው ሰው ይህንንም መጽሐፍ ጽፎ ይሆናል የሚል ግምት አለ፤ ጊዜውም በስምንተኛው ምዕተ ዓ.ቅ.ክ ሳይሆን አይቀርም :: (ከ1ነገ መግቢያ "ጸሐፊው፣ ምንጩና የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ)::

### ታሪካዊ ዳራው

ነቢዩ ዮናስ ባገለገለበት ዘመን በግማሽ ምእተ ዓመት ጊዜ ውስጥ (800-750 ዓ.ቅ.ክ) ዳግማዊ ኢዮርብዓም (793-753 ዓ.ቅ.ክ)፣ ከአንድ መቶ ዓመት በላይ በእስራኤልና በደማስቆ መካከል የነበረውን ጦርነት በድል በማጠናቀቅ በሰሜናዊው የእስራኤል መንግሥት ምድር ታላቅ ጀብዱ ሠራ፤ የእስራኤልንም ታሪካዊ ድንበር መለሰ:: ኢዮርብዓም እግዚአብሔር ረድቶት (2ነገ 14፥26-27) አሦር በ797 በወቅቱ የሶርያን ኀይል በማድቀቅ፣ በደማስቆ ላይ የተቀዳጀውን ድል ተጠቅሞበታል:: ከዚያን ጊዜ በፊት ግን የእስራኤል የግዛት መጠን ከማነሱም በላይ፣ የደማስቆ ንጉሥ በሰሜኑ (2ነገ 13፥7) መንግሥት የውስጥ ጉዳይ ገብቶ ይቆጣጠር ነበር:: ይሁን እንጂ አሦር በ797 በደማስቆ ላይ ከዘመተች በኋላ የእስራኤል ንጉሥ ዮአስ በደማስቆ ንጉሥ የተወሰደውን ግዛት አስመልሶ ነበር (2ነገ 13፥25):: በአሦር የተፈጠረው የውስጥ ችግር ዳግማዊ ኢዮርብዓም የእስራኤልን ሰሜናዊ የድንበር ግዛቶች ሙሉ ለሙሉ ለማስመለስ አስችሎታል:: ይህም እንኳ ሆኖ አሦር በዚህ ጊዜ በሰሜን በኩል የሚያስፈራ መንግሥት ሆኖ ቆይቶአል::

ይህን ሁኔታ አስመልክተው የእግዚአብሔር ነቢያት ለእስራኤል ይናገሩ ነበር:: በ797 ዓ.ቅ.ክ ገደማ ኤልሳዕ በደማስቆ ላይ ስለሚገኘው ድል ለእስራኤል ንጉሥ ተናግሮ ነበር (2ነገ 13፥14-19):: ከጥቂት ዓመታት በኋላም በዳግማዊ ኢዮርብዓም የተከናወነውን ድንበር የማስመለስ ጉዳይ አስመልክቶ ዮናስ ትንቢት ተናግሮአል (2ነገ14፥25)፤ እስራኤል ድል ካደረገች በኋላ ብዙ ሳይቈይ ባገኘችው ተጨማሪ የግዛት ሥልጣን ከመጠን በላይ መደሰትና መኩራራት ጀመረች:: ኤልሳዕና ዮናስ በተናገሩት የማጽናናት ቃል መሠረት እስራኤል ከውጭ ኀይል ተጽዕኖ ተላቃ ዕረፍት አገኘች፤ እግዚአብሔር ወደ በሰጣት ታላቅ ድልና በረከት ተቀማጠለች (አሞ 6፥1)፤ ሃይማኖቷም ሌሎችን ሕዝቦች ጨለማ ሲውጣቸው እርሷ ግን በእግዚአብሔር ብርሃን የምትሆንበትን "የጌታን ቀን" በመጠባበቅ ላይ ያተኰረ ነበር (አሞ 5፥18-20)::

እግዚአብሔር ሕዝቡ እስራኤል ከደማስቆ አልፈው (አሞ 5፥27) ወደ አሦር (ሆሴ9፥3፤ 10፥6፤ 11፥5) እንዲሰደዱ ያደርጋል እንጂ ከእንግዲህ ሊታገሳቸው እንደማይችል ይነግሯቸው ዘንድ አሞጽንና ሆሴዕን የላከው (አሞ 7፥8፤ 8፥2) በዚህ ዐይነት ጊዜ ነበር:: ነነዌ ሊመጣ ካለው የእግዚአብሔር ቍጣ ትድን ዘንድ እንዲያስጠነቅቅ እግዚአብሔር ዮናስን የላከው በዚህ ጊዜ ነበር:: ዮናስ በአሞፅ ዘመን የነበረ በመሆኑ ለተጨማሪ መግለጫ ከአሞጽ መግቢያ "የተጻፈበት ቀንና ታሪካዊ ዳራው" የሚለውን ይመ::

### የተጻፈበት ጊዜ

ለአሕዛብ የተሰበከውን ስብከትና ሌሎች ምክንያቶች ስንመለከትም መጽሐፉ ከምርኮ በኋላ እንደተጻፈ ይገመታል፤ ስለዚህ በ612 ዓ.ቅ.ክ በነነዌ ላይ ከደረሰው ጥፋት በኋላ የተጻፈ ሳይሆን አይቀርም:: ይሁን እንጂ እነዚህ አስተያየቶች ይህን ያህል ወሳኝ አይደሉም:: ይህ ትረካ ኤልያስንና ኤልሳዕን በሚመለከት ከተጻፈው ጽሑፍ ጋር ተመሳሳይ እንደ ሆነ ተመልክተናል:: ይህ መጽሐፍ የተጻፈው ነነዌ ከተገለበጠች በኋላ ከሆነ፣ የነነዌን ንስሓ መግባትና እንዳትጠፋ መደረጓን መጥቀስ አስፈላጊነቱ አጠያያቂ ነው:: በስምንተኛው ምዕተ ዓመት የእግዚአብሔርን ቃል ለአሕዛብ መናገር አያስፈልግም ብሎ ማለት ቀደም ሲል በነበሩበት ምዕተ ዓመታት ኤልያስና ኤልሳዕ አገልግሎታቸውን እስከ ባዕዳን ምድር ድረስ አስፍተው እንደ ነበር አለማስተዋል ነው (1ነገ 17፥24፤ 2ነገ 8፥1-17):: አሞጽም (760-750) በዘመኑ ለአሕዛብ ብቻ ሳይሆን ለእስራኤልም የእግዚአብሔርን የትድግና ሥራ የተናገረ ነቢይ ነበር (አሞ 1፥3-2፥16፤ 9፥7:12):: ምናልባት በ8ኛው ምዕተ ዓመት መጨረሻ ላይ ይኸውም አሞጽና ሆሴዕ በይፋ የእግዚአብሔርን ቃል ለሕዝቡ ከተናገሩ በኋላ በ722-

721 ሰማርያ በአሦር እጅ ከመውደቋ በፊት ተጽፎአል የሚለው የበለጠ አሳማኝ ሳይሆን አይቀርም::

**ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ**

ይህ መጽሐፍ እንደ ብዙዎቹ የብሉይ ኪዳን የትንቢት መጽሐፎች ሳይሆን፣ በአንድ ትንቢታዊ ተልእኮ ላይ ያተኰረ ታሪክ ነው:: በዚህ ተልእኮ ላይ ማተኰሩ፣ ስለ ኤልያስና ስለ ኤልሳዕ አገልግሎት በአንደኛና በሁለተኛ ነገሥት ውስጥ ከተጻፈው ታሪክ ጋር ይመሳሰላል፤ እንደዚሁም በኢሳይያስ፣ በኤርምያስና፣ በሕዝቅኤል ውስጥ ካሉ ከተወሰኑ ታሪኮች ጋር ይቀራረባል::

አብዛኛውን ጊዜ በመጽሐፍ ቅዱስ ታሪኮች ላይ እንደሚታየው፣ ጸሐፊው ብዙውን ነገር በጥቂት ቦታ አሳጥሮ ጽፎአል፤ የመጽሐፉ ጠቅላላ ታሪክ የተገለጸው በአርባ ጥቅሶች ሲሆን፣ በተጨማሪም የዮናስን የምስጋና ጸሎት የሚገልጹ ስምንት በግጥም የተጻፉ ጥቅሶች ያካተተ ነው:: በይዘቱ ዕጥር ምጥን በማለቱ በግልጽነቱና በገጸ ባሕርይ አገላለጹ ከሩት መጽሐፍ ጋር ብዙ ይመሳሰላል::

"ድነት ከእግዚአብሔር ዘንድ ነው" የሚለው የዮናስ ዐቢይ የንስሓ ጸሎት የታሪኩ ጡዘት ነው (1፥9፤ 2፥9፤ 4፥2):: ዮናስ ከነነዌ ወጣ ብሎ በጠራራ ፀሓይ በሜዳ ላይ ተቀምጦ ሳለ በመደምደሚያው ላይ የተጠቀሰው ዐረፍተ ነገር የእግዚአብሔር ቃል የመጨረሻና ወሳኝ እንደ ሆነ ይገልጻል::

ጸሓፊው ግልጽ በሆነ መንገድ አንድን ነገር ወክሎ በማቈም ሐሳብን የመግለጽ የአጻጻፍ ሥልት ይጠቀማል:: እግዚአብሔር የእስራኤል ጠላት ለሆነችው ነነዌ ያለው ፍቅር የሚያመለክተው እግዚአብሔር ለአሕዛብ ሁሉ ያለውን ፍቅር ነው:: በአንጻሩም እምቢተኛው ዮናስ ያደረገው ነገር እስራኤል ከእግዚአብሔር ጋር ስለ አላት መልካም ግንኙነት የምትቀናና የእግዚአብሔርንም ቸርነት ለአሕዛብ ለማካፈል ፈቃደኛ ያለመሆኗን የሚገልጽ ነው::

ይህ መጽሐፍ እግዚአብሔር ለእስራኤል ሰፋ ያለ ዕቅድ እንዳለው ይገልጻል፤ ይኸውም እግዚአብሔር ለጠቅላላ ፍጥረቱ የሚገደው መሆኑን እስራኤል እንድትረዳና ይህንም ዐላማ ከግብ ለማድረስ የምትጫወተውን ሚና በሚገባ እንድታውቅ ነው::

**አስተዋፅኦ**

1. ዮናስ ከተልእኮው መሸሹ (ም 1-2)
   ሀ. ለዮናስ የተሰጠው ትእዛዝና ከዚያ መሸሹ (1፥1-3)
   ለ. ለአደጋ የተጋለጡት መንገደኞች ወደ አምላካቸው ያደረጉት ጩኸት (1፥4-6)
   ሐ. የዮናስ አልታዘዝም ባይነት ተጋለጠ (1፥6-10)
   መ. በዮናስ ላይ የተፈጸመው ቅጣትና ከጥፋት መዳኑ (1፥11-2፥1፤ 2፥10)
   ሠ. ለእግዚአሔር ያቀረበው የምስጋና ጸሎት (2፥2-9)
2. ዮናስ ሳይወድ ተልእኮውን መፈጸሙ (ም 3-4)
   ሀ. ዮናስ ወደ ነነዌ እንዲሄድ ዳግመኛ መታዘዙ፣ እርሱም ትእዛዙን መቀበሉ (3፥1-4)
   ለ. ለጥፋት የተጋለጠው የነነዌ ሕዝብ ወደ እግዚአብሔር ያደረገው የንስሓ ጸሎት (3፥5-9)
   ሐ. የነነዌ ሕዝብ ንስሓ ተቀባይነት ማግኘቱ (3፥10-4፥4)
   መ. ዮናስ ከጥፋት መዳኑ፣ የተሰጠውም ግሳጼ (4፥5-11)

## ዮናስ ከእግዚአብሔር ኰበለለ

**1** *የእግዚአብሔር ቃል ወደ አማቴ ልጅ ወደ ዮናስ እንዲህ ሲል መጣ፤* [2]“ክፋቷ በእኔ ፊት ወጥቶአልና ወደ ታላቂቱ ከተማ ወደ ነነዌ ሂደህ፣ በእርሷ ላይ ስበክ::”

[3]ዮናስ ግን *ከእግዚአብሔር ፊት* ኰበለለ፤ ወደ ተርሴስም ለመሄድ ተነሣ:: ወደ ኢዮጴ ወረደ፣ ወደዚያው ወደ ተርሴስ የምትሄድ መርከብም አገኘ:: የጕዞውንም ዋጋ ከከፈለ በኋላ፣ *ከእግዚአብሔር ፊት* ወደ ተርሴስ ለመ ኰብለል በመርከቢቱ ተሳፈረ:: [4]*እግዚአብሔርም* በባሕሩ ላይ ታላቅ ነፋስን ላከ፤ ከባድ ማዕበልም ተነሥቶ መርከቢቱን አንገላታት፤ ልትሰበርም ተቃረበች:: [5]መርከበኞቹ ሁሉ ፈሩ፤ እያንዳንዱም ሰው ወደ አምላኩ ጮኸ፤ የመርከቢቱም ክብደት እንዲቀል፣ በውስጧ የነበረውን ዕቃ ወደ ባሕሩ ጣሉት::

ዮናስ ግን ወደ መርከቢቱ ታችኛ ክፍል ወርዶ ተኛ፤ በከባድም እንቅልፍ ላይ ነበር:: [6]የመርከቢቱም አዛዥ ወደ እርሱ ሄዶ፣ “እን ዴት ትተኛለህ? ተነሥና ስምህ ከህን ጥራ፤ እንጂ ምናልባትም ያስበንና ከጥፋት ያድነን ይሆ ናል” አለው::

[7]ከዚያም መርከበኞቹ እርስ በርሳቸው፣ “ይህ ክፉ ነገር በማን ምክንያት እንደ መጣብን ለማ ወቅ፣ ኑ፣ ዕጣ እንጣጣል” ተባባሉ::

1፥1 2ነገ14፥25፤ ማቴ12፥39-41፤ 16፥4፤ሉቃ11፥29-32
1፥2 ዘፍ10፥11፤ ናሆ1፥1
1፥3 ዘፍ10፥4፤ ዘፀ4፥13፤ኢሱ19፥46፤ መዝ139፥7፤ ኤር20፥9፤አሞ3፥8፤ ሐሥ9፥36:43
1፥4 መዝ107፥23-26
1፥5 ሐሥ27፥1819
1፥6 መዝ107፥28፤ ዮና3፥8
1፥7 ዘኁ32፥23፤ ኢሱ7፥10-18፤1ሳሙ 14፥42፤ምሳ16፥33

1፥1 *የእግዚአብሔር ቃል...መጣ፤* 3፥1 ይመ፤ ነቢዩ ለተቀ በለው መገለጥ መለኮታዊ ምንጭ እንዳለው የሚያመለክት ሐረግ ነው (ለምሳሌ 1ነገ 17፥8፤ ኤር 1፥2:4፤ ሆሴ1፥1፤ኢል 1፥1፤ ሐጌ 1፥1:3፤ ዘካ1፥1:7 ይመ):: *ዮናስ፤* ከመግቢያው፣ “የመጽሐፉ ርእስና ጸሐፊው” የሚለውን ይመ::

1፥2 *ታላቂቱ ከተማ፤* 3፥2፤ 4፥11 ይመ:: እንዲሁም የ3፥3 ማብ ይመ:: በዘፍ10፥11-12 መሠረት በመጀመሪያ በናምሩድ ከረሆቦት ኢር፣ ከካለህና ከሬሲን ጋር አንድ ላይ ሳትሠራ አት ቀርም፤ በዘመኑ በነበረው ትውፊት መሠረትም፣ በ612 ዓ.ቅ.ክ እስከ ወደቀችበት ጊዜ ድረስ “ታላቂቱ ከተማ” ተብላ ትታወቅ ነበር:: (ከናሆም መጽሐፍ መግቢያ “ታሪካዊ ዳራው” የሚለውን ይመ) በ700 ዓ.ቅ.ክ ገደማ ሰናክሬም የአሦር ዋና ከተማ አደረጋት:: ዮናስ ተወልዶ ካደገባት ከተማ ከጋት ሔፌር 800 ኪሎ ሜትር ያህል ትርቅ ነበር:: *ክፋቷ በእኔ ፊት ወጥቶአልና፤* ከሰዶምና ከገሞራ ጋር ያወዳድሩ (ዘፍ 18፥20-21):: ከነነዌ ዐመፅ በቀር (3፥8)፣ “ክፉ መንገዳቸው” (3፥8:10) በዮናስ መጽሐፍ ላይ አልተገለጸም:: በኋላ ግን ናሆም የነነዌ ኀጢአት በእግዚአብሔር ላይ ክፋትን ማሤር (ናሆ 1፥11)፣ በጦርነት ጊዜም ጭከናና ዝርፊያ (ናሆ2፥12-13፤ 3፥1:19)፣ ዝሙት አጋሪነትና ጥንቈላ (ናሆ 3፥4) እንዲሁም በንግድ አጭበርብሮ መበዝበዝ እንደ ነበር ገልጾአል (ናሆ 3፥16)::

1፥3 *ኰበለለ፤* የዚህ ምክንያት በ4፥2 ተገልጾአል:: ከእግዚ አብሔር ለመኰብለል መሞከር ከንቱ እንደ ሆነ በመዝ 139፥7-9-10 ተጠቅሶአል:: *ተርሴስም፤* ምናልባት በደቡብ ምዕራብ ስፔን የምትገኘው የታርቴሰስ ከተማና ከጂብራልተር አጠገብ ያለችው የፊንቃውያን የማዕድን ቅኝ ግዛት ነች:: ዮናስ፣ የዓለም ዳርቻ ነው ተብሎ ወደሚታሰበው ከነነዌ ማዶ ወዳለው አቅጣጫ በመሄድ፣ ከእግዚአብሔር ከተሰጠው መለኮታዊ ተግባር ለመሸሽ ሞከረ::

*1፥4-5፤* የዮናስ ተልእኮ ለአረማውያን ፍርድ የማይቀር መሆኑን በመግለጽ የእግዚአብሔርን የማስጠንቀቂያ ቃል መናገር ቢሆንም፣ ወደ ነነዌ አልሄድም በማለቱ እነዚህን አረማውያን መርከበኞች ጭንቅ ውስጥ ከተታቸው::

1፥4 *እግዚአብሔርም...ታላቅ ነፋስን ላከ፤* በዮናስ ተልእኮ ውስጥ የእግዚአብሔር ሉዓላዊ ሥራ በሌሎች ነገሮችም ላይ ለምሳሌ፤ ዓሣ ነባሪው (ቊ 17)፣ የዮናስ መተፋት (2፥10)፣ የወይን ተክል (4፥6)፣ ትል (4፥7)፣ እንዲሁም የምሥራቅ ነፋስ (4፥8) ተገልጾአል::

1፥5 *ወደ አምላኩ፤* ከተለያዩ ወደቦች የመጡት መርከበ ኞች የተለያዩ የጣዖት አማልክትን ማምለካቸው ግልጽ ነው::

1፥6 *የመርከቢቱም አዛዥ ወደ እርሱ ሄዶ፤* አረማዊው የመርከብ አዛዥ በመርከቢቱ ላሉት ሁሉ ግድ መሰኘቱ፣ በእግዚአብሔር ከሚያምነው የእግዚአብሔርን ማስጠንቀቂያ ለነነዌ ለመናገር እንቢተኛ ከሆነው ነቢይ ጋር የሚነጻጸር ነው::

1፥7 *ኑ፣ ዕጣ እንጣጣል፤* በቅርብ ምሥራቅ አገሮች ዕጣ መጣጣል በስፋት የተለመደ ሥርዐት ነበር:: ትክክለኛው ዘዴ ግልጽ ባይሆንም፣ አብዛኛውን ጊዜ ከዕቃ ውስጥ ዕንጨቶችን ወይም ምልክት የተ



*ዕጣም ተጣጣሉ፤ ዕጣውም በዮናስ ላይ ወደቀ።*

[8]ከዚያም፣ "ይህ ሁሉ አስጨናቂ ነገር በማን ምክንያት እንደ መጣብን ንገረን፤ ሥራህ ምንድን ነው? ከወዴትስ መጣህ? አገርህስ የት ነው? ከየትኛውስ ሕዝብ ነህ?"አሉት።

[9]እርሱም፣ "እኔ ዕብራዊ ነኝ፤ የብስንና ባሕርን የፈጠረውን፣ የሰማይን አምላክ እግዚ አብሔርን አመልካለሁ" አለ።

[10]እርሱ አስቀድሞ ነግሮአቸው ስለ ነበር፣ *ከእግዚአብሔር* እንደ ኰበለለ ዐወቁ፣ ስለዚህም በሁኔታው በመደንገጥ፣ "ይህ ያደረግኸው ምንድን ነው?" አሉት።

[11]የባሕሩም ማዕበል እጅግ እየበረታ ስለ ሄደ፣ "ባሕሩ ጸጥ እንዲልልን በአንተ ላይ ምን ብናደርግ ይሻላል?" አሉት።

[12]እርሱም፣ "ይህ ታላቅ ማዕበል በእኔ ምክንያት እንደ መጣባችሁ ዐውቃለሁ፤ አንሥታችሁ ወደ ባሕሩ ጣሉኝ፤ ባሕሩም ጸጥ ይላል" አላቸው።

[13]ሰዎቹ ግን ባላቸው ኀይል እየቀዘፉ ወደ የብስ ለመጠጋት ሞከሩ፤ ይሁን እንጂ አልቻሉም፤ ባሕሩ የባሰ ይናወጥ ነበርና። [14]"*እግዚአብሔር* ሆይ፤ እባክህ በዚህ ሰው ነፍስ ምክንያት አታጥፋን፤ የዚህ ንጹሕ ሰው ደምም በእኛ ላይ አይሁን፤ *እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተ የወደድኸውን አድርገሃልና" ብለው ወደ *እግዚአብሔር* ጮኹ። [15]ከዚያም ዮናስን ይዘው ወደ ባሕሩ ጣሉት፤ ባሕሩም ከመና ወጥ ጸጥ አለ። [16]ሰዎቹም *እግዚአብሔርን* እጅግ ፈሩ፤ *ለእግዚአብሔር* መሥዋዕትም አቀረቡ፤ ለእርሱም ስእለትን ተሳሉ።

[17]*እግዚአብሔር* ግን ዮናስን የሚውጥ ትልቅ ዓሣ አዘጋጀ፤ ዮናስም በዓሣው ሆድ ውስጥ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት አደረ።

**የዮናስ ጸሎት**

**2** ዮናስ በዓሣው ሆድ ውስጥ ሆኖ ወደ አምላኩ ወደ *እግዚአብሔር* ጸለየ፤

[2]እንዲህም አለ፤

"ተጨንቄ ሳለሁ ወደ *እግዚአብሔር*
ተጣራሁ፤
እርሱም መለሰልኝ፤
ከመቃብሩም[ሀ] ጥልቅ ርዳታን ፈልጌ
ተጣራሁ፤
አንተም ጩኸቴን ሰማህ።
[3]ጥልቅ ወደ ሆነው፣
ወደ ባሕሩ መካከል ጣልኸኝ፤
ፈሳሾችም ዙሪያዬን ከበቡኝ[ለ]፤
ማዕበልህና ሞገድህ ሁሉ፣
በላዬ አለፉ።
[4]እኔም፣ 'ከፊትህ ጠፋሁ፣
ነገር ግን እንደ ገና፣
ወደ ቅዱስ መቅደስህ፣
እመለከታለሁ' አልሁ።

1፥9 ዘፍ1፥9፤ነህ 9፥6፤መዝ96፥9፤ዳን 2፥18፤ሐሥ17፥24
1፥12 2ሳሙ 24፥17፤ 1ዜና21፥17
1፥13 ምሳ21፥30
1፥14 ዘዳ21፥8፤ ዳን4፥35
1፥15 መዝ107፥29፤ ሉቃ8፥24
1፥16 ዘኍ30፥2፤ መዝ66፥1314፤ማር 4፥41
1፥17 ዩና4፥6፡7፤ ማቴ12፥40፤16፥4፤ ሉቃ11፥30
2፥2 መዝ18፥6፤ 86፥13፤120፥1፤ ሰቆ3፥55
2፥3 2ሳሙ22፥5፤ መዝ42፥7፤88፥6
2፥4 1ነገ8፥48፤ መዝ31፥22፤ኤር7፥15

[ሀ]2 የዕብራይስጡ ትርጒም ሲኦል ይላል።
[ለ]5 *"ውሃዎች በጕሮሮዬ ነበሩ"* የሚሉ አሉ

ደረገባቸውን ጠጠሮች በማውጣት ዕጣ ከሚጣልበት ጕዳይ ላይ ይጥሉ ነበር። *ዕጣውም በዮናስ ላይ ወደቀ፤* በዕጣው ፍርድ እግዚ አብሔር ወንጀለኛውን ገለጠው (ከኢያ 7፥14-26፤ ከ1ሳሙ 14፥38-44፤ ከምሳ 16፥33 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥9 *ዕብራዊ፤* የዘፍ 14፥13 ማብ ይመ። *የብስንና ባሕርን የፈጠረውን የሰማይን አምላክ፤* መርከበኞቹ ዮናስ የተናገረው ስለ ትልቅ አምላክ እንደ ሆነ ሳይረዱ አልቀረም። በጥንት ዘመን የቅርብ ምሥራቅ ሃይማኖቶች በአብዛኛው ከፍተኛው አምላክ የባሕሮች ጌታ ነው ብለው ያምኑ ስለነበር፣ በነበሩበት ሁኔታ ውስጥ የተከሡተው ነገር ይህንን እውነት አጽንቶላቸዋል (የኢሱ 3፥10 ማብ ይመ)። ይህ የዮናስ የመጀመሪያ ንስሓ ነው፤ እንደ መጀመሪያው ንስሓ ሁለተኛውም ንስሓ፣ (ከ2፥9፤ 4፥2) ፍጹም እውነት ነበር። እምነቱ ትክክል ቢሆንም እንኳ፣ ዮናስ ለነነዌ የተሰጠውን መለኮታዊ ተልእኮ ለመፈጸም እምቢተኛ ሆነ።

1፥10 *ይህ ያደረግኸው ምንድነው?* ይህ ምልስ አዘል ጥያቄ በዮናስ ላይ እንደ ክስ ይቈጠራል።

1፥12 *አንሥታችሁ ወደ ባሕሩ ጣሉኝ፤* በፍርሀት የተሸበሩትን መርከበኞች ሕይወት ለማትረፍ የዮናስ ለሞት መዘጋጀት፣ ራቅ ካለ ስፍራ ሆኖ ከተማዪቱ ስትጠፋ ለማየት ቢያንስ እንደምትጠፋ ተስፋ በማድረግ (4፥5 ይመ)፣ በልበ ደንዳናነት ካደረገው ሽሽት ጋር የሚነጻጸር ነው።

1፥13 *ባላቸው ኀይል እየቀዘፉ፤* የዕብራይስጡ አገባብ ሥራው የቱን ያህል አድካሚ መሆኑን ለማመልከት እጅግ ሥዕላዊ የሆነ አገላለጽ ያለውን ቃል ይጠቀማል፤ ይኸውም፤ "በመቅዘፊያ መቈፈር" የሚል ትርጒም አለው። መርከቧ በነፋስ ኀይል ወይም በመቅዘፊያ፣ አሊያም በሁለቱ ልትነዳ ትችላለች። መርከበኞቹ ዮናስን ወደ ባሕሩ ለመወርወር ማንገራገራቸው ዮናስ ነነዌ ከሚ መጣባት ፍርድ እንድትጠነቀቅ ለመናገር ፈቃደኛ ካለመሆኑ ጋር በእጅጉ የሚነጻጸር ነው።

1፥16 *እግዚአብሔርን እጅግ ፈሩ፤* መርከበኞቹ ሌሎችን አማልክት ሁሉ ያወገዙበት ምንም ማስረጃ የለም (ንዕማንን ከ2ነገ 5፥15 ጋር ያነጻጽሩ)። ጥንት የነበሩ አረማውያን የሌሎች ብዙ አማልክትን ህልዎትና ኀይል ለማስተናገድ ዝግጁ ነበሩ። ስለዚህ መርከበኞቹ ቢያንስ ያሉበት ሁኔታ በእስራኤል አምላክ ቍጥጥር ሥር እንደሆነ፤ እርሱ ማዕበሉን እንዳስነሣና ጸጥ እንዳደረገ፣ በዚህ ሁኔታ ውስጥ ሊታወቅና ሊሰገድለት የሚገባው እርሱ መሆኑን ተገንዝበዋል።

1፥17 *እግዚአብሔር...አዘጋጀ፤* ይህ ባሕርይ ጎላጭ የሆነ ሐረግ በ4፥6-8 ላይም ይገኛል። *ትልቅ ዓሣ፤* በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው የዕብራይስጡ ቃልና በማቴ 12፥40 የተጠቀሰው የግሪክ ቃል ትልቅ ዓሣን በሚያሳይ መልክ በጥቅሉ የተገለጸ በመሆኑ፣ የግድ ዓሣ ነባሪን አያመለክትም። ይህ ትልቅ ዓሣ በአሞ 9፥3 ከተጠቀሰው ከክፉው የባሕር እባብ በጥንቃቄ ተለይቶ ተገልጾአል፤ በተረፈ "ሌዋታን" (ኢሳ 27፥1) እና "የጥልቁ አውሬ "(ኢዮ 7፥12፤ መዝ 74፥13፤ ሕዝ 32፥2 ይመ) ተብሎ ተጠርቶአል። *ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት፤* በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው ሐረግ፣ በማቴ 12፥40 ላይ እንዳለው አንድ ሙሉ ቀንንና የሌሎች ሁለት ቀኖችን ሰዓታት ጨምሮ አንድ የተወሰነ ጊዜን የሚያመለክት ነው። (የማቴ 12፥40፤ የሉቃ 9፥28፤ የ1ቆሮ 15፥4 ማብ ይመ)። ያም ሆነ ይህ አዲስ ኪዳን ዮናስ ያለፈበትን ሁኔታ፣ ሦስት ቀንና ሌሊት በመቃብር ላሳለፈው ለክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ አምሳያ አድርጎ ያቀርበዋል። (ማቴ 12፥40፤ ማቴ 16፥4፤ ሉቃ 11፥29-32 ይመ)።

2፥2-9፤ በባሕር ውስጥ እያለ እንዳይሞት ትድግናን ያገኘ ዘንድ የቀረበ የምስጋና መዝሙር ነው። ዮናስ ወደ ጥልቆ እየሰመጠ ሲሄድ፣ ለርዳታ የጸለየውን ጸሎት አስታወሰ። ስለፈጸመው በደል ሞት የሚገባው ቢሆንም፣ እግዚአብሔር ግን የተለየ ምሕረት እንዳደረገለት ስላወቀ፣ ለእግዚአብሔር የሚያቀርበው አክብሮት ከፍ ብሉበታል። የዚህ መዝሙር ቋንቋ፣ ዮናስ የዳዊትን የምስጋና መዝሙሮች ሥነ ጽሑፍ ጠንቅቆ እንደሚያውቅ ያመለክታል።

2፥2 *ከመቃብሩም፤* ዮናስ በባሕር ውስጥ የሞት ያህል እንደተሰማው የሚያመለክት ዘይቤያዊ አነጋገር ነው (መዝ 18፥5፤ 30፥3 ይመ)፤ የዘፍ 37፥35 ማብ ይመ።

2፥3 *ጣልኸኝ...ማዕበልህና፤* ዮናስ መርከበኞቹ (1፥15) የእግ ዚአብሔር ፍርድ ማስፈጸሚያ መሣሪያዎች መሆናቸውን ተገን ዝቦአል።

2፥4 *ነገር ግን እንደገና ወደ ቅዱስ መቅደስህ እመለከ ታለሁ፤* ተመሳሳይ የሆነ በተስፋ የመጠባበቅ ሁኔታ በዳዊት የጸሎት መዝሙሮችም ውስጥ ይገኛል (ለምሳሌ መዝ 5፥7፣ 27፥4)። በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው፣ "ቤተ መቅደስ" በኢየሩሳሌም ያለውን ቤተ መቅደስ የሚያመለክት ይመስላል፤ በቍ 7 የተጠቀሰው ግን በሰ ማይ ያለውን የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ የሚያመለክት

[5]ውሃ እስከ ዐንገቴ አጠለቀኝ፤
ጥልቁም ከበበኝ፤
የባሕርም ዐረም በራሴ ላይ ተጠመጠመ።
[6]ወደ ተራሮች መሠረት ሰመጥሁ፤
የምድርም በር ለዘላለም ተዘጋብኝ፤
*እግዚአብሔር* አምላኬ ሆይ፤
አንተ ግን ሕይወቴን ከጕድጓድ አወጣህ።
[7]"ነፍሴ በዛለች ጊዜ፣
*እግዚአብሔር* ሆይ፤ አንተን ዐሰብሁ፤
ጸሎቴም ወደ አንተ፣
ወደ ቅዱስ መቅደስህ ዐረገች።
[8]"ከንቱ በሆኑ ጣዖቶች ላይ የሚንጠለጠሉ፣
ሊያገኙ የሚገባቸውን ጸጋ ያጣሉ።
[9]እኔ ግን በምስጋና መዝሙር፣
መሥዋዕት እሠዋልሃለሁ፤
የተሳልሁትንም እሰጣለሁ፤
ድነት *ከእግዚአብሔር* ዘንድ ነው።"
[10]*እግዚአብሔርም* ዓሣውን አዘዘው፤ ዮናስንም በደረቅ ምድር ላይ ተፋው።

## ዮናስ ወደ ነነዌ ሄደ

**3** *የእግዚአብሔርም* ቃል ለሁለተኛ ጊዜ እንዲህ ሲል ወደ ዮናስ መጣ፤

[2]"ወደ ታላቂቱ ከተማ ወደ ነነዌ ሄደህ የምነግርህን መልእክት ስበክላት።"

[3]ዮናስም *የእግዚአብሔርን* ቃል ታዘዘ፤ ወደ ነነዌም ሄደ። በዚህ ጊዜ ነነዌ ታላቅ ከተማ ነበረች፤ እርሷንም ከዳር እስከ ዳር ለመጐብኘት ሦስት ቀን ያስፈልግ ነበር። [4]ዮናስም ወደ ከተማዪቱ ገብቶ የመጀመሪያውን ቀን ከተጓዘ በኋላ "ነነዌ በአርባ ቀን ውስጥ ትገለበጣለች" ብሎ ዐወጀ። [5]የነነዌም ሰዎች እግዚአብሔርን አመኑ፤ ጾምንም ዐወጁ፤ ሰዎቹም ሁሉ ከትልቁ እስከ ትንሹ ማቅ ለበሱ።

[6]ወሬውም ወደ ነነዌ ንጉሥ በደረሰ ጊዜ፣ ከዙፋኑ ወረደ፤ ልብሱንም አወለቀ፤ ማቅም ለብሶ በዐመድ ላይ ተቀመጠ። [7]ከዚያም እንዲህ ሲል በነነዌ ዐዋጅ አስነገረ፤

"ከንጉሡና ከመሳፍንቱ የወጣ ዐዋጅ፤

ማንም ሰው ወይም እንስሳ፣ የከብት መንጋም ሆነ የበግ መንጋ፣ ምንም ነገር አይቅመስ፤ አይብላ፤ ውሃም አይጠጣ። [8]ነገር ግን ሰውም እንስሳም ማቅ ይልበስ፤ ሁሉም አጥብቆ ወደ እግዚአብሔር ይጮኽ፤ ሰዎችም ሁሉ ክፉ መንገዳቸውንና የግፍ ሥራቸውን ይተዉ። [9]እኛ እንዳንጠፋ እግዚአብሔር ራርቶ ከጽኑ ቍጣው ይመለስም እንደ ሆነ ማን ያውቃል?"

[10]እግዚአብሔርም ምን እንዳደረጉና ከክፉ መንገዳቸውም እንዴት እንደ ተመለሱ ባየ ጊዜ ራራላቸው፤ በእነርሱም ላይ ሊያመጣ ያሰበውን ጥፋት አላደረገም።

## ዮናስ እግዚአብሔር ምሕረት በማድረጉ ተቈጣ

**4** ዮናስ ግን ፈጽሞ አልተደሰተም፤ ስለዚህም ተቈጣ። [2]ወደ *እግዚአብሔርም* እንዲህ ብሎ ጸለየ፤ "*እግዚአብሔር* ሆይ፤ በአገሬ ሳለሁ የተናገርሁትስ ይህን አልነበረምን? ፈጥኜ ወደ ተርሴስ ለመኰብለል የተነሣሁትም ለዚሁ ነበር፤ አንተ ቸርና ርኅሩኅ፣ ምሕረትህ የበዛ ከቍጣ የራቅህ አምላክ፣ ጥፋትንም ከማምጣት የምትመለስ እንደ ሆንህ ዐውቃለሁ። [3]አሁንም *እግዚአብሔር* ሆይ፤ ነፍሴን ውሰድ፤ ከምኖር መሞት ይሻለኛልና።"

[4]*እግዚአብሔር* ግን፣ "በውኑ ልትቈጣ ይገባሃልን?" አለው።

[5]ዮናስም ከከተማዪቱ ወጥቶ በስተ ምሥራቅ በአንድ ስፍራ ተቀመጠ። በዚያም ለራሱ ዳስ ሠራ፤

2፥5 መዝ69፥12
2፥6 ኢዮ17፥16፤ 28፥9፤33፥18፤ መዝ30፥3
2፥7 2ዜና30፥27፤ መዝ11፥4፤18፥6፤ 77፥11-12
2፥8 ዘዳ32፥21፤ 1ሳሙ12፥21
2፥9 ዘፀ15፥2፤ዘኍ 30፥2፤መዝ3፥8፤42፥4 ፤50፥14፡23፤116፥14፤ መክ5፥45፤ዕብ13፥15
3፥1 ዮና1፥1
3፥4 ኤር18፥7-10
3፥5 ዳን9፥3፤ማቴ 11፥21፤12፥41፤ሉቃ 11፥32
3፥6 አስ4፥13፤ ኢዮ2፥8፡13፤ ሕዝ27፥30-31
3፥7 2ዜና20፥3፤ ዕዝ10፥6
3፥8 ኢዮ16፥17፤ መዝ130፥1፤ኤር 7፥3፤25፥5፤ና1፥6
3፥9 2ሳሙ12፥22፤ መዝ85፥3፤ኤር18፥8፤ ኢል2፥14
3፥10 ዘፀ32፥14፤ ኤር18፥8፤አሞ7፥6
4፥1 ቍ4፤ ማቴ20፥11፤ሉቃ 15፥28
4፥2 ዘፀ22፥27፤ዘኍ 14፥18፤ዘዳ4፥31፤ መዝ86፥5፡15፤103፥8 ፤ኤር20፥7፤ ኢል2፥13
4፥3 ዘኍ11፥15፤ ኢዮ7፥15፤ኤር8፥3
4፥4 ዘፍ4፥6፤ ማቴ20፥11-15

---

ነው። እስራኤላውያን እነዚህን ሁለት የእግዚአብሔር ማደሪያዎች ሳይነጣጥሉ ይመለከቱአቸዋል (1ነገ 8፥38-39 ይመ)።

2፥6 *ከጕድጓድ፤* ከመቃብር ለማለት ነው (የቍ 2 ማብ ይመ፣እንዲሁም መዝ 30፥3 ይመ)።

2፥9 *የተሳልሁትንም፤* በመዝሙረ ዳዊት መጽሐፍ ውስጥ ጸሎቶች በአብዛኛው የምስጋና መሥዋዕትን በያዙ ስእለቶች የታጀቡ ናቸው (ለምሳሌ መዝ 50፥14፤ 56፥12፤61፥8፤65፥1፤66፥13-14፤ 116፥12-19)። *ድነት ከእግዚአብሔር ዘንድ ነው፤* ዮናስ በከፍተኛ ደረጃ ያቀረበው የምስጋና ጸሎት ነው። ይህ የዮናስ ሁለተኛ የንስሓ ቃል ሲሆን (የ1፥9 ማብ ይመ)፣ የመጽሐፉ ሥነ ጽሑፋዊ ማእከል ነው።

3፥2 *የምነግርህን መልእክት ስበክላት፤* ነቢይ የእግዚአብሔርን መልእክት የሚያቀርብ እንጂ በቅድሚያ ስለሚመጣው ሁኔታ የሚናገር አይደለም።

3፥3 *ታዘዘ፤* ይታዘዝ እንጂ የነነዌ ሰዎች እንዲጠፉ ይፈልግ ነበር (4፥1-5)። *ታላቅ ከተማ፤* ከተማዪቱ ከ120,000 የሚበልጡ ኗሪዎች እንደነበሩባት የሚናገረውን 4፥11 ይመ። የሥነ ቅርስ ተመራማሪዎች ቍፋሮ ኋለኛዪቱ የነነዌ የንጉሥ ከተማ ዙሪያዋ 12ኪ.ሜ ያህል እንደነበር ያመለክታል። ሆኖም፣ "ለመጐብኘት ሦስት ቀን ይወስዳል" የሚለው አባባል ሰፊ ቦታን የሸፈነች ከተማ መሆኗን ያመለክታል። ይኸውም በዘፍ10፥11-12 እንደ ተጠቀሰው አራቱን ከተሞች ማለትም ነነዌ፣ ሬሆቦት፣ ካለህና ሬሴንን የሚያጠቃልል ሊሆን ይችላል። የታላቋ የነነዌ ከተማ ዙሪያዋ 96 ኪሎ ሜትር ይሸፍናል። በሌላም በኩል፣ "ሦስት ቀን" የሚለው አባባል የመካከለኛ ርዝመት ርቀትን ለመግለጽ የሚውል የተለመደ አባባል ሳይሆን አይቀርም (ዘፍ 30፥36፤ ዘፀ 3፥18፣ኢሱ 9፥16-17 ይመ)።

3፥5-6 *ጾምንም ዐወጁ ... ማቅ ለበሱ...በዐመድ ላይ ተቀመጠ፤* በንስሓ ራስን የማዋረድ የተለመደ ምልክት ነው (1ነገ 21፥27፤ ነህ 9፥1 ይመ)።

3፥5 *እግዚአብሔርን አመኑ፤* የነነዌ ሰዎች በእውነት ወደ እግዚአብሔር ተመልሰዋል ማለት ሊሆን ይችላል (ከማቴ 12፥41 ጋር ያነጻጽሩ)። በሌላ በኩል በእግዚአብሔር ማመናቸው መርከበኞቹ ከነበራቸው ፈሪሀ እግዚአብሔር (የ1፥16 ማብ ይመ) ይህን ያህል የጠለቀ ላይሆን ይችላል። ቢሆንም ግን የነቢዩን ማስጠንቀቂያ ሰምተው ርምጃ ወስደዋል።

3፥6 *ወደ ነነዌ ንጉሥ፤* የአሦር ንጉሥ ነው።

3፥8፤ የቤት እንስሳትን መጨመር የተለመደ አልነበረም፤ የነነዌ ሰዎች የእግዚአብሔርን ምሕረት በአስቸኳይ እንደፈለጉም ይገልጻል።

3፥9፤ እግዚአብሔር ንስሓ ለሚገባ ሰው ሊመጣ ያለውን ቅጣት በማስቀረት ዘወትር ምሕረት ያደርጋል።

4፥1 *ተቈጣ፤* እግዚአብሔር ለእስራኤል ጠላት በመራራቱ ዮናስ እጅግ ተቈጣ። እግዚአብሔር በጎነቱን ለእስራኤል ብቻ እንጂ ለአሕዛብ እንዲገልጥ አልፈለገም።

4፥2 *ርኅሩኅ፤ ምሕረትህ የበዛ፤* ዘፀ 34፥6-7 ማብ ይመ። ዮናስ የተለመደውን የንስሓ አኳለጽ ሥርዐት ይከተላል (የ1፥9 ማብ ይመ)። *ከቍጣ የራቅህ፤* በአንጻሩ ግን ዮናስ ፈጥኖ ተቈጥቶአል (ቍ 19)።

4፥3 *ነፍሴን ውሰድ፤* ነቢዩ ኤልያስ በ1ነገ 19፥4 ከተናገረው ጋር ያነጻጽሩ። እግዚአብሔር ምሕረቱን ለነነዌ ቢገልጥ ዮናስ እስራኤል በእግዚአብሔር ዘንድ ያላትን ተወዳጅነት የምታጣ መሰለው። ከጥቂት ጊዜ በፊት ዮናስ ትድግናን በማግኘቱ ተደስቶ ነበር፤ አሁን ግን ነነዌ ስላልጠፋች ሞትን ተመኘ።

4፥5 *ዳስ፤* ይህ ዳስ ከስጠው ጥላ ይልቅ በሚቀጥለው ቍጥር እንደተጠቀሰው እግዚአብሔር ያዘጋጀው ቅል የበለጠ ጥላ እንደሚሰጥ

በከተማዪቱም የሚሆነውን ለማየት ከዳሱ ጥላ ሥር ተቀመጠ። [6]*እግዚአብሔር* አምላክም የቅል ተክል አብቅሎ፣ የዮናስ ራስ ጥላ እንዲያገኝና ሙቀትም እንዳያስጨንቀው ከበላዩ እንዲያድግ አደረገ፣ ዮናስም ስለ ቅሉ እጅግ ደስ አለው። [7]ነገር ግን በሚቀጥለው ቀን በማለዳ እግዚአብሔር ትል አመጣ፤ ትሉም ቅሉን በላ፤ ቅሉም ደረቀ። [8]ፀሓይ ስትወጣ፣ እግዚአብሔር የሚያቃጥል የምሥራቅ ነፋስ አመጣ፤ ፀሓዩም የዮናስን ራስ አቃጠለ፤ እርሱም ተዝለፈለፈ፤ መሞትም ፈልጎ፣ 'ከመኖር መሞት ይሻለኛል" አለ።

[9]እግዚአብሔር ግን ዮናስን፣ "በውኑ ስለ ቅሉ ልትቈጣ ይገባሃልን?" አለው።

እርሱም፣ "በእርግጥ እስከ ሞት ልቈጣ ይገባኛል" አለ።

[10]*እግዚአብሔር* ግን እንዲህ አለው፤ "አንተ እንዲበቅል ወይም እንዲያድግ ላልደከምክበት ለዚህ ቅል እጅግ አዝነሃል፤ በአንድ ሌሊት በቀለ፤ በአንድ ሌሊትም ደረቀ። [11]ታዲያ፣ እኔ ቀኝና ግራቸውን ለይተው መናገር የማይችሉ፣ ከአንድ መቶ ሃያ ሺህ በላይ ሰዎችና አያሌ እንስሶች ለሚኖሩባት ለታላቋ ከተማ ለነነዌ ማዘን አይገባኝምን?"

4፥6 ዮና1፥17
4፥7 ኢል1፥12
4፥8 1ነገ19፥4
4፥9 ቍ4
4፥11 ዮና1፥2፤ 3፥2፡10

ተገልጾአል። የሚሆነውን ለማየት፤ ዮናስ አሁንም የነነዌን መጥፋት ተስፋ ያደርግ ነበር።

4፥6 *እግዚአብሔር አምላክም ... አደረገ* ይህ ባሕርይ ገጥሞ ሐረግ በተጨማሪ በቍ 7-8፣ 1፥17 ላይም ይገኛል። *የቅል ተክል፤* ዘይት ከሚሰጡ ተክሎች አንዱ ሆኖ፣ ዐሥራ ሁለት ጫማ ያህል ከፍታና ሰፋፊ ቅጠሎች ያሉት ትንሽ ዛፍ ሊሆን ይችላል። እግዚአብሔር በምሕረቱ፣ እልኸኛና ልበ ደንዳና ለሆነው ለእርሱ ነቢይ ምቾትን አበዛለት።

4፥8 *መሞት ይሻለኛል፤* የቍ 3 ማብ ይመ።

4፥10 *በአንድ ሌሊት በቀለ፤ በአንድ ሌሊትም ደረቀ፤* አሁን ታይቶ ወዲያው የሚጠፋን ነገር የሚያመለክት ነው።

4፥11 *ቀኝና ግራቸውን ለይተው መናገር የማይችሉ፤* እንደ ትንንሽ ልጆች (ከዘዳ 1፥39፤ ከኢሳ7፥15-16 ጋር ያነጻጽሩ) የነነዌ ሰዎች የእግዚአብሔር የአባትነት ርኅራኄ ያስፈልጋቸዋል። *አያሌ እንስሶች፤* የእግዚአብሔር ርኅራኄ ለቤት እንስሳትም ጭምር ነው። *ማዘን አይገባኝምን?* እግዚአብሔር በመጽሐፉ መጀመሪያ ላይ እንደ ተናገረ ሁሉ (1፥1)፣ ከዚህም ላይ በመጨረሻ ይናገራል። ለዮናስ የሰጠው ተልእኮ ለነነዌ ሰዎች ያሳየውን ምሕረትና ርኅራኄ የሚያመለክት ሲሆን፣ ለዮናስ የተነገረው የመጨረሻው ቃል ደግሞ እግዚአብሔር ለሰውና ለእንስሳ ማለትም ለፍጥረት ሁሉ ግድ መሰኘቱን በአጽንዖት የሚያመለክት ነው። "እግዚአብሔር ሆይ፤ አንተ ሰውንም እንስሳትንም ታድናለህ" (መዝ 36፥6፣ ነህ 9፥6፣ መ145፥16 ይመ)፤ ይህም ብቻ ሳይሆን፣ "ከመንገዳቸው ተመልሰው በሕይወት እንዲኖሩ እንጂ በክፉዎች ሞት ደስ አልሰኝም" (ሕዝ 33፥11፣ ሕዝ 18፥21-23 ይመ) ብለሃል። ከጥንት ጀምሮ ዮናስና የአገሩ ሰዎች እግዚአብሔር ለእስራኤል ባለው ልዩ ምሕረት ደስ ሲሰኙ በአንጻሩ በጠላቶቻቸው ላይ እንዲደርስ የሚመኙት የእርሱን ቍጣ ብቻ ነው፤ በዚህ ስፍራ እግዚአብሔር እንዲህ ዐይነቱን ደንዳናነት በመንቀፍ የእርሱን የተትረፈረፈ ደግነት ያውጃል። እንዲህ ዐይነቱን ጥንካሬና ክፉት በዚህ ስፍራ ሲገሥጽ፣ የራሱን ምሕረትና በጎነት ግን በይፋ ይናገራል።

# ትንቢተ ሚክያስ

***መግቢያ***

***ጸሓፊው***

ከራሱ ከመጽሐፉና በኤር 26፥18 ላይ ከተጠቀሰው ውጭ፣ ስለ ነቢዩ ሚክያስ ብዙ የሚታወቅ ነገር የለም:: እርሱም ሞሬት ከምትባል ከተማ የመጣ ሰው ነበር (1፥1)፤ ይህ ከተማ ምናልባት ሞሬሼትጌት የምትባለዋ ከተማ ራሷ ሳትሆን አይቀርም:: ትንቢቱም በሚክያስ ዘመን በኅብረተ ሰቡ ዘንድ ይታይ የነበረው ምግባረ ብልሹነት፣ በተለይ በትናንንሽ ከተሞችና እርሱ በተወለደባት አካባቢ እየተስፋፋ በመምጣቱ፣ ሚክያስ በዚህ የተሰማውን ጥልቅ የሐዘን ስሜት የሚገልጽ ነው::

***የተጻፈበት ጊዜ***

ሚክያስ ትንቢት የተናገረው በ750 እና በ686 ዓ.ቅ.ክ መካከል ባለው ጊዜ፣ በይሁዳ ነገሥታት በኢዮአታም፣ በአካዝና በሕዝቅያስ (1፥1፤ኤር26፥18) ዘመነ መንግሥት ነው:: ስለዚህ ሚክያስ፣ ኢሳይያስና (ኢሳ 1፥1ይመ) ሆሴዕ (ሆሴ 1፥1ይመ) በኖሩበት ዘመን የነበረ ሰው ነው:: ሚክያስ በ722-721 የተፈጸመውን የሰማርያን ውድቀት (1፥6) በሚመለከት ትንቢት ተናግሮአል:: ይህም የቀድሞው የሚክያስ አገልግሎት የተጀመረው በኢዮአታምና (750-732) በአካዝ (735-715) ዘመነ መንግሥት መሆኑን ይጠቍማል:: የሚክያስ መልእክት በሕዝቅያስ ዘመን ከተደረገው ሃይማኖታዊ ተሐድሶ በፊት የነበረውን ማኅበራዊ ሁኔታ ያንጸባርቃል (2ነገ 18፥9 እንዲሁም የኢሳ 36፥1 ማብ ይመ)::

***ታሪካዊ ዳራው***

ሚክያስ በኢየሩሳሌም ስለ ነበረው የፖለቲካ ሕይወት የኢሳይያስን ያህል መረዳት ያለው ባይመስልም፣ የመጽሐፉ ታሪካዊ መሠረት ከኢሳይያስ መጽሐፍ የመጀመሪያው ክፍል ጋር ይመሳሰላል:: ይህም የሆነው ምናልባት ሚክያስ እንደ አሞጽ ከይሁዳ መንደር የመጣ ሰው በመሆኑ ነው::

እስራኤል የቀድሞ እምነቷን ችላ ያለችበት ጊዜ ነበር:: ሚክያስ፣ የእስራኤል ዋና ከተማ ሰማርያ እንደምትወድቅና (1፥5-7)፣ ይሁዳም ባድማ መሆኗ የማይቀር ስለመሆኑ (1፥9-16) ትንቢት ተናግሮአል:: በዚህ ጊዜ ሦስት ዐበይት ታሪካዊ ነገሮች ተከናውነዋል:-

1. በ734-732 ዓ.ቅ.ክ የአሦር ንጉሥ ኃያሉ ቴልጌልቴልፌልሶር በሶርያ፣ በጋዛ በተወሰኑ የእስራኤል ግዛቶችና በይሁዳ ላይ ዘምቶአል፤ አስቀሎናና ጋዛ ድል ተደርገዋል፤ ይሁዳ፣ አሞን፣ ኤዶምና ሞዓብ ለአሦር ንጉሥ ገብረዋል፤ እስራኤል ግን አልገበረችም:: በ2ነገ 15፥29 ላይ እንደ ተጠቀሰው፣ የሰሜኑ መንግሥት ገለዓድንና ከገሊላ አውራጃ ይበልጡን ክፍል ጨምሮ አብዛኛውን ግዛቱን አጥቶአል:: ደማስቆ በ732 ወድቃ፣ ከአሦር ግዛት ጋር እንድትቀላቀል ተደርጋለች::
2. በ722-721 ሰማርያ ወደቀች፤ የእስራኤል ሰሜናዊ ግዛትም ድል ተደርጎ በአሦር ተያዘ::
3. ይሁዳ በ701 አሦርን በመቃወም በተደረገው ዐመፅ ተካፋይ ሆነች፤ ከዚህም የተነሣ በንጉሥ ሰናክሬምና በወታደሮቹ ተወረረች፤ ይሁን እንጂ ኢየሩሳሌም ሳትወረር ቀርታለች::

***ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ***

የሚክያስ የአጻጻፍ ዘዬ ከኢሳይያስ አጻጻፍ ጋር ተመሳሳይ ነው:: ሁለቱም ነቢያት ጠንካራ ቃልና ዘይቤአዊ አነጋገሮችን ይጠቀማሉ፤ ሁለቱም ሰዎች አስፈሪ ስለ ሆነው ቅጣትና ተስፋ ሰጪ ስለ ሆነው ፍትሕ ትልቅ ትኵረት አድርገዋል:: ሚክያስ በአንድ ድምፀት ከአንድ በላይ ትርጕም በሚሰጡ ቃላት መጫወትን ያዘወትራል (1፥10-15 አግራጭ ትርጕሙን ይመ)::

***መሪ ሐሳቡና መልእክቱ***

በአስተዋፅኦው ላይ እንደ ተመለከተው፣ የሚክያስ መልእክት ጥፋት አዘል ወይም ተስፋ ሰጭ የትንቢት ቃላት የሚፈራረቁበት ነው:: የመልእክቱም መሪ ሐሳብ የእግዚአብሔርን ፍርድና ማዳኑን የሚያመለክት ነው:: እግዚአብሔር የጣዖት አምልኮን ፣ ፍትሕ ማጓደልን ዐመፀኝነትንና የባዕድ የአምልኮ ሥርዐትን እንደሚጠላ፣ ነገር ግን ንስሓ በሚገባው ሰው ደስ እንደሚለው ሚክያስ በአጽንዖት ይገልጻል:: የዳዊት መንግሥት ማብቂያው የተቃረበ ሲመስል፣ ሊመጣ ባለው አዳኝና መሲሕ እጅግ የገነነ ይሆናል::

***አስተዋፅኦ***

1 ርእሳዊ መግለጫ (1፥1)

2 በእስራኤልና በይሁዳ ላይ የተነገረው ፍርድ (1፥2-3፥12)

 ሀ. መግቢያ (1፥2)

 ለ. የተተነበየው ጥፋት (1፥3-7)

 ሐ. ስለሚደርሰው ጥፋት ወዮታ (1፥8-16)

መ. በሚክያስ ዘመን በነበረው ኅብረተሰብ የታየው ምግባረ ብልሹነት (2፥1-11)
ሠ. በጨለማ ውስጥ የተስፋ ፍንጣቂ (2፥12-13)
ረ. በአለቆች ላይ የተሰጠ ፍርድ (ም 3)
3 ስለ እስራኤልና ስለ ይሁዳ የተነገረ ተስፋ (ም 4-5)
ሀ. ወደ ፊት የሚመጣው መንግሥት (ም 4)
ለ. ሊመጣ ያለው ንጉሥ (5፥1-5)
ሐ. የእግዚአብሔር ሕዝብ ድል እንደሚያገኝ (5፥5-15)
4 እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር ያለው ሙግት (ም 6)
ሀ. እግዚአብሔር በእስራኤል ላይ ያቀረበው ክስ (6፥1-8)
ለ. የሚመጣው ፍርድ (6፥9-16)
5 ተስፋ መቍረጥ ወደ ድል እንደሚቀየር (ም 7)
ሀ. ሚክያስ ስለ ኅብረተ ሰቡ ምግባረ ብልሹነት ማዘኑ (7፥1-6)
ለ. ሚክያስ የነበረው አስተማማኝ ተስፋ (7፥7)
ሐ. ወደ ፊት የእግዚአብሔር ሕዝብ የሚጠብቀው ብሩህ ተስፋ (7፥8-13)
መ. የእግዚአብሔር መንግሥት ድል አድራጊነት (7፥14-20)

**1** በይሁዳ ነገሥታት በኢዮአታም፣ በአካዝና በሕዝቅያስ ዘመን ወደ ሞሬታዊው ወደ ሚክያስ የመጣው *የእግዚአብሔር* ቃል፣ ስለ ሰማርያና ስለ ኢየሩሳሌም ያየው ራእይ ይህ ነው፤

2 እናንተ አሕዛብ ሆይ፤ ሁላችሁም ስሙ፤
ምድር ሆይ፤ በውስጧም የምትኖሩ ሁሉ አድምጡ፤
ጌታ ከቅዱስ መቅደሱ፣
ልዑል *እግዚአብሔር* በእናንተ ላይ ይመሰክርባችኋል።

**በሰማርያና በኢየሩሳሌም ላይ የተላለፈ ፍርድ**

3 እነሆ፤ *እግዚአብሔር* ከመኖሪያ ስፍራው ይመጣል፤
ወርዶም በምድር ከፍታዎች ላይ ይራመዳል።
4 ተራሮች ከሥሩ ይቀልጣሉ፤
ሸለቆዎችም ይሰነጠቃሉ፤
በእሳት ፊት እንዳለ ሰም፣
በገደል ላይ እንደሚወርድ ፈሳሽ ይሆናሉ።
5 ይህ ሁሉ የሚሆነው ስለ ያዕቆብ በደል፣
ስለ እስራኤልም ቤት ኀጢአት ነው።
የያዕቆብ በደል ምንድን ነው?
ሰማርያ አይደለችምን?
የይሁዳስ የኰረብታ መስገጃ ምንድን ነው?
ኢየሩሳሌም አይደለችምን?

6 "ስለዚህ ሰማርያን የፍርስራሽ ክምር፣
ወይን የሚተከልባትም ስፍራ አደርጋታለሁ፤
ድንጋዮቿን ወደ ሸለቆ አወርዳለሁ፤
መሠረቷንም ባዶ አደርጋለሁ።
7 ጣዖቶቿ ሁሉ ይሰባበራሉ፤
ለቤተ መቅደሷ የቀረበው ገጸ በረከት በእሳት ይቃጠላል፤
ምስሎቿን ሁሉ እደመስሳለሁ፤
ገጸ በረከቷን በዝሙት አዳሪነት እንደ ሰበሰበች ሁሉ፣
አሁንም ገጸ በረከቷ የዝሙት አዳሪነት ዋጋ መቀበያ ይሆናል።

**ልቅሶና ሐዘን**

8 በዚህ ምክንያት አለቅሳለሁ፤ ዋይ ዋይም እላለሁ፤
ባዶ እግሬንና ዕርቃኔን እሄዳለሁ፤
እንደ ቀበሮ አላዝናለሁ፤
እንደ ጒጒትም አቃስታለሁ።
9 ቊስሏ የማይሽር ነውና፤
ለይሁዳ ተርፎአል፤
እስከ ሕዝቤ መግቢያ በር፣
እስከ ኢየሩሳሌም እንኳ ደርሶአል።
10 በጌት[ሀ] አታውሩት፤
ከቶም አታልቅሱ[ለ]፤
በቤትዓፍራ[ሐ]፣

1፥1 ቊ14፤ 1ዜና3፥12፡13፤ ኢሳ1፥1፤ ኤር26፥18፤ሆሴ1፥1
1፥2 ዘዳ31፥50፤ ዘዳ4፥26፤32፥1፤ መዝ11፥4፤50፥7፤ ኢሳ1፥2፤ኤር6፥19
1፥3 ኢሳ18፥4፤ 64፥1፤አሞ4፥13
1፥4 ዘኍ16፥31፤ ኢዮ9፥5፤መዝ46፥2፤ ናሆ1፥5
1፥5 አሞ8፥14
1፥6 ዘዳ20፥6፤ ሕዝ13፥14፤አሞ5፥11
1፥7 ዘፀ32፥20፤ ዘዳ9፥21፤23፥17-18፤ ሕዝ6፥6
1፥8 ኢሳ15፥3፤ 20፥2
1፥9 2ነገ18፥13፤ ኢሳ3፥26፤ ኤር10፥19፤46፥11

[ሀ]10 'ጌት' የሚለው ቃል በዕብራይስጡ 'አውራ' ከሚለው ጋር ተመሳሳይ አነባበብ አለው። [ለ]10 ዕብራይስጡ ከዚህ ጋር ሲስማማ፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም ግን 'በአኮ ላይ አታልቅሱ' ይላል። 'በአኮ' የምለው የዕብራይስጡ ቃል 'አለቀሰ' ከሚለው የዕብራሱ ቃል ጋር ተመሳሳይ አነባበብ አለው። [ሐ]10 'ቤት ዓፍራ' ትርጒሙ 'የትቢያ ቤት' ማለት ነው።

1፥1 *ሚክያስ*፤ የስሙ ትርጒም፣ "እንደ እግዚአብሔር ያለ ማን ነው?" ማለት ነው። *ሞሬታዊው*፤ ከመግቢያው "ጸሓፊው" የሚለውን ይመ። *በኢዮአታም በአካዝና በሕዝቅያስ*፤ ከመግቢያው "የተጻፈበት ዘመን" የሚለውን ይመ። የእነዚህን ነገሥታትና የሚክያስን መጽሐፍ ታሪካዊ ዳራ በተመለከተ 2ነገ 15፥32-16፥20፤ 18-20 ይመ። ኢሳይያስ፣ ሆሴዕና ሚክያስ ትንቢት የተናገሩት ከሞላ ጐደል በተመሳሳይ ዘመን ነበር (ኢሳ 1፥1፣ ሆሴ 1፥1 ይመ)። *ራእይ*፤ ኢሳ 1፥1 እና ማብ ይመ። *ስለ ሰማርያና ስለ ኢየሩሳሌም*፤ የእስራኤል (የሰሜኑ መንግሥት) እና የይሁዳ (የደቡቡ መንግሥት) ዋና ከተሞች ናቸው። ሚክያስ የተናገረው ፍርድ፣ የሚመለከተው ዋና ከተሞቹን ብቻ ሳይሆን፣ በውስጣቸው የሚኖረውን ሕዝብ ጭምር ነው።

1፥2 *ስሙ*፤ በዕብራይስጡ ይህ ቃል በተጨማሪ በምዕ3፥1 እና 6፥1 "አድምጡ" ተብሎ የተተረጐመውን፣ እነርሱን አስመልክቶ የተነገረውን ትንቢት ያስተዋውቃል (እንዲሁም 3፥9፤6፥2 ይመ)። *አሕዛብ...ምድር*፤ እግዚአብሔር ሕዝብን ሁሉ ለፍርድ በሚጠራበት ጊዜ፣ የእግዚአብሔር ቀን የቀረበ መሆኑን የሚያመለክት ማሳሰቢያ ነው። ሚክያስ ያችን ቀን እየተመለከተ፣ በእስራኤልና በይሁዳ ላይ ፍርዱ አይቀሬ መሆኑን በትንቢቱ ይናገራል። *ከቅዱስ መቅደሱ*፤ በመዝ 11፥4 በዮና 2፥7፤ በዕን 2፥20 እንደተገለጸው መንግሥተ ሰማያትን ያመለክታል (ቊ 3 ይመ)።

1፥3 *እግዚአብሔር... ይመጣል*፤ እግዚአብሔር በታሪክ ውስጥ ጣልቃ እንደሚገባ የሚያመለክት የብሉይ ኪዳን የተለመደ አገላለጽ ነው (መዝ 18፥9፤96፥13፤144፥5፣ ኢሳ 26፥21፤31፥4፤ 64፥1-3 ይመ)። *ከፍታዎች*፤ ተራሮችን ወይም የአረማውያንን ቤተ ጣዖቶች የሚያመለክት ሊሆን ይችላል። ከዚህ ላይ ሁለቱም ተጠቅሰዋልና (ቊ 4-5)፤ ከአሞ 4፥13 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥4 *ተራሮች...ይቀልጣሉ*፤ መዝ 97፥5፣ ናሆ 1፥5 ይመ።

1፥5 *ስለ ያዕቆብ*፤ ያዕቆብ የእስራኤል ተለዋጭ ስም ነው (ዘፍ 32፥28 እና ማብ ፤ 35፥10 ይመ)። *እስራኤልም*፤ በዚህ ስፍራና በቊ 13 የሚያመለክተው በተለይ የሰሜኑን መንግሥት ሲሆን፣ ሚክያስ ግን ለደቡቡ መንግሥት (3፥1፣8-9፣ 5፥1:3 ይመ) ወይም ለመላው የቃል ኪዳን ሕዝብ (ቊ 14፥15፣ 2፥12፣ 5፥1፤ 6፥2 ይመ) ተጠቅሞበታል። *የኰረብታ መስገጃ*፤ የአረማውያንን የጣዖት አምልኮ ማእከል የሚያመለክት ነው (2ዜና 28፥25 ይመ)።

*1፥6-7*፤ በዚህ ስፍራ ተናጋሪው እግዚአብሔር ነው። ይህ የትንቢት ቃል በሚክያስ ዘመን አሦራውያን ሰማርያን በ722-721 ዓ.ቅ.ክ. ባወደሙበት ጊዜ ተፈጽሞአል (2ነገ 17፥6)።

1፥6 *ወደ ሸለቆ*፤ የሰማርያ ከተማ የተቈረቈረችው በኰረብታ ላይ ነበር (1ነገ 16፥24)።

1፥7 *በዝሙት አዳሪነት*፤ አብዛኛውን ጊዜ ዝሙት አዳሪነት በብሉይ ኪዳን የጣዖት አምልኮ ወይም የመንፈሳዊ ታማኝነት ጒድለት ምልክት ነው (ዘፀ 34፥15-16፤ መሳ 2፥17፤ ሕዝ 23፥29-30)። *ዋጋ*፤ ሰማርያ በጣዖት አምልኮ የሰበሰበችውን ሀብት አሦራውያን ወስደው፣ በአማልክቶቻቸው ቤተ መቅደስ ውስጥ ዳግም ለጣዖት አምልኮ ተጠቅመውበታል።

1፥8 *በዚህ*፤ የሚመጣውን የሰማርያን መጥፋት የሚያመለክት ነው። *ባዶ እግሬንና*፤ የሐዘን ምልክት ነው (2ሳሙ 15፥30)። ሚክያስ ባዶ እግሩንና ዕርቃኑን በኢየሩሳሌም ከተማ የተጓዘበት ሁኔታ ሳይኖር አይቀርም (ከኢሳ 20፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። *ዕርቃኔን*፤ በወገቡ ላይ ብቻ ጨርቅ ታጥቆ ነበር።

1፥9 *ቊስሏ*፤ ሰማርያ በወረራ እንደምትያዝ የተነገረ ፍርድ ነው። *የማይሽር*፤ ኢሳ 17፥11 እና ማብ፣ ኤር 30፥12 ይመ። *በር*፤ አሦራውያን በሰሜኑ መንግሥት ላይ የሚያደርሱት ጥፋት እስከ ኢየሩሳሌም በር ድረስ እንደሚተላለፍ በሽታ ይሰራጫል ማለት ነበር (ቊ 12)። በር በዚያ ዘመን የከተማዋ የአስተዳደር ሥራ የሚከሄድበት ስፍራ ነበር (ዘፍ 19፥1 እና ማብ፣ ሩት 4፥1-4 ይመ)።

*1፥10-15*፤ በአማርኛ ትርጒሙ ላይ በተለያየ መንገድ ሊብራሩ የሚችሉ ቃላት ተገልጸዋል። በሼፌላህ አጠገብ አሉ ተብለው የተጠቀሱት ከተሞች ማለትም በተራራ ግርጌ (500-1500 ጫማ ከፍታ ያላቸው)፣ በሜድትራኒያን ጠረፍ በይሁዳ ተራሮች መካከል ይገኛሉ።

1፥10 *በጌት አታውሩት*፤ እነዚህ ቃላት በይሁዳ ላይ ስለሚደረገ የቀብር ልቅሶ የሚያመለክቱ ናቸው። ሚክያስ በጌት የሚኖሩ አረማውያን በእግዚአብሔር ሕዝብ መውደቅ እንዲደሰቱ

በትቢያ ላይ ተንከባለሉ::
11 እናንት በሻፊር[መ] የምትኖሩ፣
ዕራቃናችሁን ሆናችሁ በኀፍረት ዕለፉ፤
በጸዓናን[ሠ] የሚኖሩ
ከዚያ አይወጡም፤
ቤትዔጼል በሐዘን ላይ ናት፤
ለእናንተም መጠጊያ ልትሆን አትችልም::
12 ከመከራው መገላገልን በመሻት፣
በማሮት[ረ] የሚኖሩ በሥቃይ ይወራጫሉ፤
እስከ ኢየሩሳሌም በር ሳይቀር፣
ክፉ ነገር *ከእግዚአብሔር* ዘንድ
መጥቶአልና::
13 እናንት በለኪሶ[ሰ] የምትኖሩ፣
ፈረሶችን ከሠረገላው ጋር አያይዙ፤
ለጽዮን ሴት ልጅ፣
የኀጢአት መጀመሪያ እናንት ነበራችሁ፤
የእስራኤል በደል
በእናንተ ዘንድ ተገኝቶአልና::
14 ስለዚህ እናንተ ለሞሬሼትጌት፣
ማጫ ትሰጣላችሁ፤
የአክዚብ[ሸ] ከተማ፣
ለእስራኤል ነገሥታት መታለያ
ትሆናለች::
15 እናንት በመሪሳ[ቀ] የምትኖሩ
ድል አድራጊ አመጣባችኋለሁ፤
ያ የእስራኤል ክብር የሆነው
ወደ ዓዶላም ይመጣል::
16 ደስ ለምትሰኙባቸው ልጆቻችሁ፣
በሐዘን ራሳችሁን ተላጩ፤
ራሳችሁን እንደ አሞራ ራስ ተመለጡት፤
ከእናንተ በምርኮ ይወሰዳሉና::

## የእግዚአብሔርና የሰው ዕቅድ

**2** ክፉ ለመሥራት ለሚያቅዱ፣
በመኝታቸው ሳሉ ተንኰል
ለሚያውጠነጥኑ ወዮላቸው!
ሲነጋ በማለዳ ይፈጽሙታል፤
የሚያደርጉበት ኀይል በእጃቸው ነውና::
2 ዕርሻ ይመኛሉ፤ ይይዙታልም፤
ቤት ይመኛሉ፤ ይወስዱታልም፤
የሰውን ቤት፣
የባልንጀራን ርስት አታልለው ይወስዳሉ::
3 ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"እነሆ፤ በዚያ ሕዝብ ላይ ጥፋት ላመጣ
ዐቅጃለሁ፤
ከዚህም ለማምለጥ አትችሉም::
ከእንግዲህ በትዕቢት አትመላለሱም፤
የመከራ ጊዜ ይሆናልና::
4 በዚያ ቀን ሰዎች ይሣለቁባችኋል፤
በሐዘን እንጕርጕሮ እንዲህ እያሉ
ያፌዙባችኋል፤
'እኛ ፈጽሞ ጠፍተናል፤
የወገኔ ርስት ተከፋፍሎአል::
ከእኔ ነጥቆ ወስዶ፣
ዕርሻዎቻችንን ላሸነፉን አከፋፈለ::'
5 ስለዚህ *በእግዚአብሔር* ጉባኤ ውስጥ፣
መሬት በዕጣ የሚያካፍል ማንም
አይኖርም::

## ሐሰተኞች ነቢያት

6 ነቢያቶቻቸው፣ "ትንቢት አትናገሩብን፤
ስለ እነዚህ ነገሮች ትንቢት አትናገር፤
ውርደት አይደርስብንም" ይላሉ::
7 የያዕቆብ ቤት ሆይ፤ እንዲህ ሊባል ይገባልን?
"*የእግዚአብሔር* መንፈስ የማይታገሥ ነውን?

1፥11 ሕዝ23፥29
1፥12 ኤር14፥19፤ 40፥2
1፥13 ኢሱ10፥3፤ መዝ9፥14
1፥14 ቍ1፤ ኢሱ15፥44፤ 2ነገ16፥8፤ ኤር15፥18
1፥15 ኢሱ12፥15፤ 15፥44
1፥16 ዘሌ13፥40፤ ዘዳ4፥27፤ኢዮ1፥20፤አሞ5፥27
2፥1 1ሳሙ29፥20፤ መዝ36፥4
2፥2 1ሳሙ8፥14፤ ምሳ30፥14፤ ኢሳ1፥23፤5፥8፤ ሕዝ46፥18
2፥3 ኢሳ2፥12፤ ኤር18፥11፤አሞ3፥1-2
2፥4 ዘሌ26፥31፤ ኤር4፥13፤6፥12
2፥5 ዘኍ34፥13፤ ዘዳ32፥13፤ኢሱ18፥4
2፥6 መዝ44፥13፤ ኤር18፥16፤19፥8፤ 25፥18፤29፥18፤ ሚክ6፥16
2፥7 መዝ15፥2፤ 84፥11፤119፥65

[መ]11 'ሻፊር' ትርጕሙ አስደሳች ማለት ነው:: [ሠ]11 'ጸዓናን' የሚለው ቃል በዕብራይስጡ 'ውጣ' ከሚለው ጋር ተመሳሳይ አነባበብ አለው:: [ረ]12 'ማሮት' የሚለው ቃል በዕብራይስጡ 'መራራ' ከሚለው ጋር ተመሳሳይ አነባበብ አለው:: [ሰ]13 'ለኪሶ' የሚለው ቃል በዕብራይስጡ ቡድን ከሚለው ጋር ተመሳሳይ አነባበብ አለው:: [ሸ]14 'አክዚብ' ትርጕሙ አታላይ/ማታለል ማለት ነው:: [ቀ]15 'መሪሳ' የሚለው ቃል በዕብራይስጡ 'ድል አድራጊ' ከሚለው ጋር ተመሳሳይ አነባበብ አለው::

አልፈለገም፤ ከ2ሳሙ 1፥20 ጋር ያነጻጽሩ:: *በትቢያ ላይ ተንከባለሉ*፤ ከሚመጣው አስከፊ ጥፋት የተነሣ የሚሆነውን ሐዘን መግለጫ ምልክት ነው፤ ኢሳ 47፥1 እና ማብ ይመ::

1፥11 *ዕርቃናችሁን...በሐፍረት*፤ ወደ ፊት እስረኞች ሲሆኑ የሚገጥማቸውን ሁኔታ ያመለክታል (ኢሳ 20፥4 ይመ):: *ከዚያ አይወጡም*፤ በወረራው ምክንያት ሕዝቡ ከቤታቸው ውጭ ለመንቀሳቀስ አይደፍሩም::

1፥12 *መጥቶአልና*፤ ሚክያስ የወደፊቱን በግልጽ ተመልክቶአል፤ ለእርሱ የታየውም አሁኑኑ እንደ ተፈጸመ ዐይነት ነበር::

1፥13 በለኪሶ፤ በይሁዳ ካሉት ትልልቅ ከተሞች አንዱ ነው (ኢሳ 36፥2 እና ማብ ይመ):: በኋለኛው ዘመን ሰናክሬም ይህችን ከተማ በመያዙ ተኵራርቶ ነበር፤ ከዚህ የተነሣም ባደረገው ነገር በመርካቱ በነነዌ የነበረውን ቤተ መንግሥቱንና ያከናወነውን ዘረፋ በሚያሳዩ ሥዕሎች አስጊጦት ነበር:: *ፈረሶችን ... አያይዙ*፤ ማምለጥ እንድትችሉ ለማለት ነው:: *ለጽዮን ሴት ልጅ*፤ ኢየሩሳሌምንና ነዋሪዎቿን በሰውኛ ዘይቤ የሚገልጽ ነው::

1፥14 *ማጫ ትሰጣላችሁ*፤ በ1ነገ 9፥16 ላይ ይህ ሐረግ በዕብራይስጡ፣ "የጋብቻ ስጦታ" ተብሎ ተተርጕሞአል:: አባት ልጁ በምታገባበት ጊዜ የጋብቻ ስጦታ እንደሚሰጣት ሁሉ፣ ኢየሩሳሌም ሞሬሼትጌትን መስጠት አለባት:: *የአክዚብ* አግራጭ ትርጕሙን ይመ:: "አታላይ" የሚለው የቃሉ ትርጕም በኤር 15፥18 ላይ በበጋ የሚደርቀውን ምንጭ ለመግለጽ ተጠቅሶአል:: ልክ እንደዚህ ምንጭ፤ የአክዚብ ከተማ መኖር ያከትማል ማለት ነው:: *ለእስራኤል*፤ የ1፥5 ማብ ይመ::

*1፥15*፤ ከቍ 6-7 እንደተገለጸው ሚክያስ አሁንም እግዚአብሔርን ወክሎ ይናገራል:: *የእስራኤል ክብር*፤ እግዚአብሔር ራሱ ነው (1ሳሙ 15፥29 ይመ):: *ወደ ዓዶላም ይመጣል*፤ በፍርድ ይመጣል ማለት ነው::

*1፥16*፤ እስራኤል ከ722-721 ዓ.ቅ.ክ በአሦራውያን በምርኮ ተወሰዱ፤ ይሁዳም እንዲሁ በ586 ዓ.ቅ.ክ. በባቢሎናውያን በምርኮ ተወሰዱ::

*2፥1-5*፤ በቀጥታ የሚመለከተው ድኾችን የሚጨቍኑ ሀብታም የመሬት ከበርቴዎችን ነው::

2፥1 *የሚያደርጉበት ኀይል*፤ ጨቋኝ ሀብታሞች የኀብረተሰባቸውን የሥልጣን መዋቅር ስለተቈጣጠሩ፣ በድኾች ጫንቃ ሀብት ማካበትን ቀጠሉ::

2፥2 *ይመኛሉ*፤ ዐሥረኛውን ትእዛዝ በመተላለፍ ነው (ዘፀ 20፥17 እና ማብ ዘዳ 5፥21 ይመ):: *ርስት*፤ የአንድ ቤተ ሰብ ቋሚ ንብረት የሆነውን መሬት ያመለክታል፤ በዘሌ 25፥10፡13 (የኢዮቤልዩ ዓመት)፣ በዘኍ 27፥1-11፤36፥1-12 (የሰለጰዓድ ሴት ልጆች)፣ 1ነገ 21፥1-19 (የናቡቴ የወይን እርሻ) የሚለውን ይመ::

2፥3 ስለዚህ፤ በእስራኤል ባሉ ኀያላን ኀጢአት የተነሣ፣ ጥፋት እንደሚመጣባት የሚያመለክት ነው:: *ጥፋት*፤ አይቀሬ የሆነ ስደት ነው::

2፥4 *እኛ...ከእኔ*፤ የእግዚአብሔር ፍርድ የሚመጣባቸውን ሀብታም የመሬት ከበርቴዎች ያመለክታል:: *ወስዶ* (እርሱ)፤ እግዚአብሔርን ያመለክታል:: *ላሸነፉን*፣ ምድራቱን አሸንፈው የሚይዙትን ከሓዲ አሦራውያን (ኢሳ 33፥1 እና ማብ ይመ) ያመለክታል::

2፥5 *መሬት በዕጣ የሚያካፍል...ማንም*፤ የቃል ኪዳኑን ሕዝብ ተስፋ ሁሉ አይካፈሉም::

2፥6 *ነቢያቶቻቸው*፤ ቃላቸው ወደ ሚክያስ የደረሰውን ሐሰተኞች ነቢያት ነው::

እንዲህ ያሉት ነገሮችንስ ያደርጋልን?"
"መንገዱ ቀና ለሆነ፣
ቃሌ መልካም አያደርግምን?
[8]በመጨረሻ በሕዝቤ ላይ ጠላት ሆናችሁ
ተነሣችሁ፤
የጦርነት ሐሳብ ሳይኖራቸው፣
በሰላም ከሚያልፉ ሰዎች ላይ፣
ማለፊያ መጐናጸፊያ ገፈፋችሁ::
[9]ከሚወዱት ቤታቸው፣
የሕዝቤን ሴቶች አስወጣችኋቸው፤
ክብሬን ከልጆቻቸው፣
ለዘላለም ወሰዳችሁ::
[10]ተነሡና፤ ከዚያ ሂዱ፤
ይህ ማረፊያ ቦታችሁ አይደለምና፤
ምክንያቱም ረክሶአል፤
ክፉኛም ተበላሽቶአል::
[11]ሐሰተኛና አታላይ ሰው መጥቶ፣
'ስለ ብዙ የወይን ጠጅና ስለሚያስክር
መጠጥ ትንቢት እነግራችኋለሁ' ቢል፣
ለዚህ ሕዝብ ተቀባይነት ያለው ነቢይ
ይሆናል::

## የትድግና ተስፋ

[12]"ያዕቆብ ሆይ፤ በእርግጥ ሁላችሁንም
እሰበስባለሁ፤
የእስራኤልንም ትሩፍ በአንድነት
አመጣለሁ፤
በጕረኖ ውስጥ እንዳሉ በጎች
በመሰማሪያ ላይ እንዳለ መንጋ በአንድነት
እሰበስባቸዋለሁ፤
ቦታውም በሕዝብ ይሞላል::
[13]የሚሰብረው ወጥቶ በፊታቸው ይሄዳል፤
እነርሱም በሩን በመስበር ወጥተው
ይሄዳሉ፤
እግዚአብሔር እየመራቸው፣
ንጉሣቸው ቀድሞአቸው ይሄዳል::

## መሪዎችና ነቢያት ተገሠጹ

**3** ከዚያም እኔ እንዲህ አልሁ፤
"እናንት የያዕቆብ መሪዎች፤
እናንት የእስራኤል ቤት ገዦች ስሙ፤
ፍትሕን ማወቅ አይገባችሁምን?
[2]መልካሙን ጠላችሁ፤ ክፉውንም ወደዳችሁ፤
የሕዝቤን ቈዳ ገፈፋችሁ፤
ሥጋቸውንም ከዐጥንቶቻቸው ለያችሁ፤
[3]የሕዝቤን ሥጋ በላችሁ፤
ቈዳቸውን ገፈፋችሁ፤
ዐጥንቶቻቸውንም ሰባበራችሁ፤
በመጥበሻ እንደሚጠበስ፣
በድስት እንደሚቀቀል ሥጋ ቈራረጣችኋቸው::
[4]እነርሱም ወደ እግዚአብሔር ይጮኻሉ፤
እርሱ ግን አይመልስላቸውም፤
ካደረጉት ክፋት የተነሣ፣
በዚያ ጊዜ ፊቱን ከእነርሱ ይሰውራል::

[5]እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤

"ሕዝቤን የሚያስቱ ነቢያት፣
ሰው ሲያበላቸው፣ 'ሰላም አለ' ይላሉ፤
ሳያበላቸው ሲቀር ግን፣
ጦርነት ሊያውጁበት ይነሣሉ::
[6]ስለዚህ ሌሊቱ ያለ ራእይ፣
ጨለማውም ያለ ንግርት ይመጣባችኋል፤
በነቢያት ላይ ፀሐይ ትጠልቅባቸዋለች፤
ቀኑም ይጨልምባቸዋል::
[7]ባለ ራእዮች ያፍራሉ፤
ንግርተኞችም ይዋረዳሉ፤
ሁሉም ፊታቸውን ይሸፍናሉ፤
ከእግዚአብሔር መልስ የለምና::"

[8]እኔ ግን፣
ለያዕቆብ በደሉን፣
ለእስራኤልም ኀጢአቱን እነግር ዘንድ፣
ኀይልን፣ በእግዚአብሔር መንፈስ፣
ፍትሕና ብርታት ተሞልቻለሁ::
[9]እናንት የያዕቆብ ቤት መሪዎች፣
እናንት የእስራኤል ቤት ገዦች፣
ፍትሕን የምትንቁ፤
ትክክለኛ የሆነውንም ነገር ሁሉ
የምታጣምሙ፤ ስሙ፤
[10]ጽዮንን ደም በማፍሰስ፣
ኢየሩሳሌምን በክፋት የምትገነቡ፤ ስሙ::
[11]መሪዎቿ በጉቦ ይፈርዳሉ፤
ካህናቷ ለዋጋ ሲሉ ያስተምራሉ፤
ነቢያቷም ለገንዘብ ሲሉ ይናገራሉ::
ነገር ግን በእግዚአብሔር ላይ
ተደግፈውም፣
"እግዚአብሔር በመካከላችን አይደለምን?

2፥9 ኤር10፥20
2፥10 ዘሌ18፥25-29፤ዘዳ12፥9፤መዝ106፥38-39፤ሰቆ4፥15
2፥11 ዘሌ10፥9፤ 2ዜና36፥16፤ ኢሳ30፥10፤ኤር5፥31
2፥12 ነህ1፥9፤ ሚክ4፥7፤5፥7፤7፥18
2፥13 ኢሳ52፥12፤ 60፥11
3፥1 ኤር5፥5
3፥2 መዝ53፥4፤ ሕዝ22፥27
3፥3 ኢዮ24፥14፤ መዝ14፥4፤ ሕዝ11፥7፤24፥4-5፤ 34፥4
3፥4 ዘዳ1፥45፤ 31፥17፤1ሳሙ8፥18፤ ኢዮ15፥31፤ ኢሳ58፥4፤ ኤር11፥11፤ሕዝ8፥18
3፥5 ኢሳ3፥12፤ 9፥16፤53፥6፤ኤር4፥10
3፥6 ኢሳ8፥19-22፤ 29፥10፤ሕዝ7፥26፤ 12፥24፤አሞ8፥11
3፥7 ዘሌ13፥45፤ ሕስ6፥12፤ ኢሳ44፥25፤ ኤር6፥15፤ ሕዝ20፥3፤ሚክ7፥16
3፥8 ኢሳ57፥12፤ 61፥2
3፥9 መዝ58፥1-2፤ ኢሳ1፥23
3፥10 ኢሳ59፥7፤ ኤር22፥13፡17፤ ሕዝ22፥27፤ ሚክ7፥2፤ናሆ3፥1፤ ዕን2፥12
3፥11 ዘፀ23፥8፤ ዘሌ19፥15፤ ኢሳ1፥23፤ 10፥20፤56፥11፤ ኤር6፥13፤7፥4፤ ሰቆ4፥13፤ሕዝ13፥9፤ 34፥2፤ሆሴ4፥8፡18፤ ሚል2፥9

*2፥7*፤ ከቍ 6-7 ያሉት ጥቅሶች የተነገሩት በሚክያስ ሲሆን፣ ከቍ 7ለ-13 ያሉት ደግሞ የተነገሩት በእግዚአብሔር ነው::

2፥10 *ማረፊያ ቦታችሁ*፤ ሰዎች በሰላምና በጸጥታ የሚቀመጡበት፣ እንደግል ቦታ የሚቈጠር ስፍራ ነው (ከኢሱ 1፥13-15፤21፥43-44፤22፥4 ጋር ያነጻጽሩ)::

*2፥11*፤ ስለ ትልቅ ሀብት ብዙ ተስፋ የሚናገር ማንኛውም ሰው አድማጭ ያገኛል::

*2፥12-13*፤ እስራኤላውያን በምርኮ ተነድተው ቢሄዱም እንኳ፣ ቅሬታዎቹ ተመልሰው ይመጣሉ (የኢሳ 1፥9 ማብ ይመ)::

2፥12 *ያዕቆብ...የእስራኤልንም*፤ መላውን ሕዝብ ማለትም ሰሜኑንና ደቡቡን ያመለክታል::

*3፥1-12*፤ ቍ 1-4 የእስራኤልን አለቆች ኀጢአት፣ ከቍ 5-7 የሐሰተኛ ነቢያትን፣ ከቍ 9-12 የአለቆችን፣ የካህናትንና የነቢያትን የሚመለከት ነው::

3፥1 *የያዕቆብ...የእስራኤል*፤ በዚህ ቦታ የተጠቀሱት ሁለት ስሞች የሚያመለክቱት ይሁዳን ነው (ቍ 9-10 ይመ)::

3፥2-3 *ቈዳቸውን ገፈፋችሁ፤...በድስት እንደሚቀቀል ሥጋ*፤ አለቆች ሕዝቡን እንዴት እንዳሠቃዩ የሚገልጹ ተከታታይ ዘይቤአዊ አነጋገሮች ናቸው::

3፥2 *መልካሙን ጠላችሁ፤ ክፉውን ወደዳችሁ*፤ ከአሞ 5፥15፣ ከሮሜ 12፥9 ጋር ያነጻጽሩ::

3፥4 ይጮኻሉ (እነርሱ)፤ አለቆችን ነው:: *አይመልስላቸውም*፤ ቍ 7 ይመ:: *ፊቱን ከእነርሱ ይሰውራል*፤ ዘዳ 31፥17 ይመ፤ ኢሳ 1፥15 እና ማብ ይመ:: አለመታዘዝ ከእግዚአብሔር መለየትን ያመጣል::

3፥5 *'ሰላም' አለ ይላሉ፤* ሚክያስ ጥፋትንና በምርኮ መጋዝ በይሁዳ ላይ እንደሚደርስ ሲተነብይ፣ ሐሰተኛ ነቢያት ደግሞ ሰላም እንደሚመጣ ይተነብዩ ነበር (ቍ 12፥4፡10 ይመ)፤ እንዲሁም ኤር 6፥13-14፤8፥10-11 ይመ)::

3፥7 *ባለ ራእዮች*፤ "ነቢያት" በጥንት ጊዜ የሚታወቁበት ስም ነው (1ሳሙ 9፥9 ማብ ይመ)

*3፥8*፤ ከሚክያስ ዋነኛ ተግባሮች አንዱ ለይሁዳ ኀጢአቷን ማሳወቅ ነበር:: *መንፈስ...ተሞልቻለሁ*፤ ነቢያት በመንፈስ የተሞሉ መልእክተኞች ናቸው (ኢሳ 48፥16 ይመ)::

ምንም ዐይነት ክፉ ነገር አይደርስብንም"
ይላሉ::
[12]ስለዚህ በእናንተ ምክንያት፣
ጽዮን እንደ ዕርሻ ትታረሳለች፣
ኢየሩሳሌም የፍርስራሽ ክምር ትሆናለች፤
የቤተ መቅደሱም ኰረብታ ዐረም
የበቀለበት ጕብታ ይሆናል::

## የእግዚአብሔር ተራራ

**4** በመጨረሻው ዘመን፣
*የእግዚአብሔር* ቤተ መቅደስ ተራራ፣
ከተራሮች ልቆ ይታያል፤
ከኰረብቶች በላይ ከፍ ይላል፤
ሕዝቦችም ወደ እርሱ ይጐርፋሉ::

[2]ብዙ አሕዛብ መጥተው እንዲህ ይላሉ፤

"ኑ፤ ወደ *እግዚአብሔር* ተራራ፣
ወደ ያዕቆብ አምላክ ቤት እንሂድ፤
በመንገዱ እንድንሄድ፣
መንገዱን ያስተምረናል::"
ሕግ ከጽዮን ይመጣል፤
*የእግዚአብሔርም* ቃል ከኢየሩሳሌም::
[3]እርሱ በብዙ ሕዝብ መካከል ይፈርዳል፤
በሩቅና በቅርብ ባሉ ኀያላን መንግሥታት
መካከል ያለውን ግጭት ያቆማል፤
ሰይፋቸውን ማረሻ፣
ጦራቸውንም ማጭድ ያደርጉታል::
አንዱ መንግሥት በሌላው መንግሥት
ላይ ሰይፍ አያነሣም፤
ከእንግዲህም የጦርነት ትምህርት አይማሩም::
[4]እያንዳንዱ ሰው በገዛ ወይኑ ሥር፣
ከገዛ በለሱም ሥር ይቀመጣል፤
የሚያስፈራቸው አይኖርም፤
*የእግዚአብሔር* ጸባኦት አፍ
ተናግሮአልና::
[5]አሕዛብ ሁሉ፣
በአማልክቶቻቸው ስም ይሄዳሉ፤
እኛ ግን *በአምላካችን* በእግዚአብሔር ስም፣
ከዘላለም እስከ ዘላለም እንሄዳለን::

## የእግዚአብሔር ዕቅድ

[6]*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"በዚያች ቀን ሽባውን እሰበስባለሁ፤
ስደተኞችንና ለሐዘን ያደረግኋቸውን፣
ወደ አንድ ቦታ አመጣለሁ::
[7]የሽባዎችን ትሩፍ፣
የተገፉትንም ብርቱ ሕዝብ አደርጋለሁ፤
ከዚያች ቀን አንሥቶ እስከ ዘላለም፣
*እግዚአብሔር* በጽዮን ተራራ በእነርሱ ላይ
ይነግሣል::
[8]አንተ የመንጋው መጠበቂያ ማማ ሆይ፤
የጽዮን ሴት ልጅ ዐምባ[a] ሆይ፤
የቀድሞው ግዛትህ ይመለስልሃል፤
የመንግሥትም ሥልጣን ለኢየሩሳሌም
ሴት ልጅ ይሆናል::"

[9]አሁንስ እንደዚህ የምትጮኺው ለምንድን
ነው?
ንጉሥ የለሽምን?
ምጥ እንደ ያዛት ሴት የተጨነቅሽው፣
መካሪሽ ስለ ጠፋ ነውን?
[10]የጽዮን ሴት ልጅ ሆይ፤
ምጥ እንደ ያዛት ሴት ተጨነቂ፤
አሁንስ ከከተማ ወጥተሽ፣
በሜዳ ላይ መስፈር አለብሽና፤
ወደ ባቢሎን ትሄጃለሽ፣
በዚያ ከጠላት እጅ ትድኛለሽ፤
*እግዚአብሔር* በዚያ፣
ከጠላቶችሽ ይታደግሻል::

[11]አሁን ግን ብዙ አሕዛብ፣
በአንቺ ላይ ተሰብስበዋል፤
እነርሱም፣ "የረከሰች ትሁን፤
ዐይናችንም ጽዮንን መዘባበቻ አድርጎ
ይያት" ይላሉ::
[12]ነገር ግን *የእግዚአብሔርን* ሐሳብ አያውቁም፤
በአውድማ ላይ እንደ ነዶ የሚሰበስባቸውን፣
የእርሱን ዕቅድ አያስተውሉም::

[13]የጽዮን ልጅ ሆይ፤ ተነሥተሽ አበራዪ፤
የብረት ቀንድ እሰጥሻለሁና፤
የናስ ሰኰና እሰጥሻለሁ፤
አሕዛብንም ታደቂያቸዋለሽ::"
በግፍ ያግበሰበሱትን ትርፍ *ለእግዚአብሔር*፣
ሀብታቸውንም ለምድር ሁሉ ጌታ
ታቀርቢያለሽ::

## ከቤተ ልሔም ገዥ እንደሚመጣ የተሰጠ ተስፋ

**5** አንቺ የጭፍሮች ከተማ ሆይ፤
ጭፍሮችሽን አሰልፊ[+]፤
ከበባ ተደርጎብናልና፤
የእስራኤልን ገዥ፣

[a]8 ወይም 'ኰረብታ'
[+]1 ወይም አንቺ የተቀጠርሽ ከተማ ሆይ፤ ቅጥርሽን አጥብቂ

3፥12 ዘሌ26፥31፤ 2ነገ25፥9፤ ኢሳ6፥11፤ ኤር17፥3፤22፥6፤52፥13፤ ሰቆ5፥18፤ሕዝ5፥14
4፥1 መዝ22፥27፤ 48፥1፤86፥9፤ኤር3፥17፤ 31፥12፤ሕዝ17፥22፤ ዳን2፥35፤ዘካ8፥3
4፥2 ዘዳ18፥18፤ መዝ25፥8-9፤ 119፥171፤ ኢሳ54፥13፤ ኤር31፥6፤ ሕዝ20፥40፤ ዘካ2፥11፤14፥16
4፥3 መዝ46፥9፤ ኢሳ11፥4፤ኢል3፥10፤ ዘካ8፥20-22፤9፥10
4፥4 ዘሌ26፥6፤ 1ነገ4፥25፤ ኢሳ1፥20፤ሕዝ39፥26
4፥5 ኢሱ24፥14-15፤ 2ነገ17፥29፤ ኢሳ26፥8፤ዘካ10፥12
4፥6 መዝ106፥47፤ ኤር31፥8፤ ሕዝ34፥13፡16፤ 37፥21፤ሶፎ3፥19
4፥7 ዘፍ12፥2፤ ኢሳ2፥2፤ዳን2፥44፤ 7፥14፤ኢል2፥32፤ ሚክ2፥12፤ ሉቃ1፥33፤ራእ11፥15
4፥8 ኢሳ1፥26፤ ዘካ9፥9
4፥9 ዘፍ3፥16፤ ኤር8፥19፤30፥6፤48፥41
4፥10 ዘዳ21፥10፤ 2ነገ20፥18፤ ኢሳ43፥14፤48፥20
4፥11 ሰቆ2፥16፤ አብ1፥12፤ሚክ7፥8
4፥12 ዘፍ50፥20፤ ኢሳ55፥8፤ ሮሜ11፥33-34
4፥13 ኢሳ21፥10፤ 23፥18፤ዳን2፥44
5፥1 ሰቆ3፥30

3፥11 በጉቦ፤ ኢሳ 1፥23፡5፥23 ይመ::

*3፥12*፤ ኢየሩሳሌም በ586 ዓ.ቅ.ክ. ተደመሰሰች:: ይህ ጥቅስ ከአንድ ክፍለ ዘመን በኋላ እንደ ገና በኤር 26፥18 ተጠቅሶአል:: ኤር 26፥19 በንጉሥ ሕዝቅያስ አማካኝነት ለተካሄደው መንፈሳዊ ተሐድሶ የሚክያስ ስብከት መሣሪያ እንደ ነበር ይጠቍማል (2ነገ 18፥1-6፤ 2ዜና 29-31 ይመ)::

*4፥1-3*፤ ከእነዚህ ጥቅሶች ጋር ተመሳሳይ ምንባብ የሆነውን የኢሳ 2፥2-4 ማብ ይመ::

4፥4 *ወይኑ…በለሱም*፤ ሰላምና ጸጥታ የሰፈነበትን የእግዚአብሔርን ግዛት የሚያመለክት ነው፤ (1ነገ 4፥25፤ዘካ 3፥10 ይመ):: *የሚያስፈራቸው አይኖርም* ፤ ሰፎ 3፥13፤ ይመ፤ ፍርሀት ያለፈ ታሪክ ይሆናል ማለት ነው::

4፥5 *በእግዚአብሔር ስም…እንሄዳለን*፤ በመታመን፣ በፍቅር፣ በመታዘዝና በጌታ መደገፍ ማለት ነው፤ ከዘካ 10፥12 ጋር ያነጻጽሩ::

4፥6 *በዚያች ቀን*፤ የመሲሑን ዘመን (ቊ 1 ይመ፣ እንዲሁም የኢሳ 2፥11፡17፡20 ማብ ይመ)::

4፥7 *ቅሬታ*፤ የእግዚአብሔርን ሕዝብ ማለት ነው (2፥12 እና የኢሳ 1፥9 ማብ ይመ)::

4፥8 *የመንጋው መጠበቂያ ማማ*፤ እረኛም ንጉሥም የነበረው የዳዊት መናገሻ ከተማ ናት:: *የቀድሞው ግዛትህ*፤ የዳዊት መንግሥት መሲሑ ሲነግሥ ትታደሳለች::

*4፥9-13*፤ ከቊ 9-10 ባለው ሚክያስ በ586 ዓ.ቅ.ክ. የሚሆነውን የመንግሥት መውደቅና የማይቀረውን በምርኮ መወሰድ እንዲሁም በ538 ዓ.ቅ.ክ የሚጀምረውን ተሐድሶ ያመለክታል:: ከቊ 11-13 በኢየሩሳሌም ውድቀት በተደሰቱት ጠላቶች ላይ የተነገረውን የፍርድ ትንቢት የሚያመለክት ነው::

*5፥1*፤ ኢየሩሳሌም ትከበባለች፤ ንጉሦችዋም ተይዘው ወደ ባቢሎን ይወሰዳሉ (የመጨረሻውን ንጉሥ የሴዴቅያስን ዐይን

ጕንጩን በበትር ይመቱታል::

[2]"አንቺ ግን፣ ቤተ ልሔም ኤፍራታ ሆይ፤
ከይሁዳ ነገዶች[ቸ] መካከል ትንሿ ብትሆኚም፣
አመጣጡ[ኀ] ከጥንት፣
ከቀድሞ ዘመን[ነ] የሆነ፣
የእስራኤል ገዥ፣
ከአንቺ ይወጣልኛል::"

[3]ስለዚህ ወላዲቱ አምጣ እስክትገላገል ድረስ፣
እስራኤል ትተዋለች፤
የተቀሩት ወንድሞቹም፣
ተመልሰው ከእስራኤላውያን ጋር ይቀላቀላሉ::

[4]*በእግዚአብሔር* ኀይል
በአምላኩ *በእግዚአብሔር* ስም ታላቅነት፣
ጸንቶ ይቆማል፤ መንጋውንም ይጠብቃል::
በዚያ ጊዜ ኀያልነቱ እስከ ምድር ዳርቻ
ስለሚደርስ፣
ተደላድለው ይኖራሉ::
[5]እርሱም ሰላማቸው ይሆናል::

## ትድግናና ጥፋት

አሦራዊ ምድራችንን ሲወር፣
ምሽጐቻችንንም ጥሶ ሲገባ፣
ሰባት እረኞችን፣
እንዲያውም ስምንት አለቆችን
እናስነሣበታለን::
[6]የአሦርን ምድር በሰይፍ፣
የናምሩድን ምድር[ፕ] በተመዘዘ ሰይፍ ይገዛሉ[ኦ]፤
አሦራዊው ምድራችንን ሲወር፣
ዳር ድንበራችንን ሲደፍር፣
እርሱ ነጻ ያወጣናል::

[7]የያዕቆብ ትሩፍ፣
በብዙ አሕዛብ መካከል
*ከእግዚአብሔር* ዘንድ እንደሚወርድ ጠል፣
በሣር ላይ እንደሚጥል ካፊያ፣
ሰውን እንደማይጠብቅ፣
የሰውንም ልጆች ተስፋ እንደማያደርግ
ሰው ይሆናል::
[8]በዱር አራዊት መካከል እንዳለ አንበሳ፣
በእግሩ እየጨፈላለቀ እንደሚሄድ፣
የሰበረውን ማንም ሊነጥቀው እንደማይችል፣
በበግ መንጋ መካከል እንዳለ፣
እንደ ደቦል አንበሳ ሁሉ፣
የያዕቆብም ትሩፍ፣ በአሕዛብ ዘንድ፣
በብዙም ሕዝብ መካከል እንደዚሁ ይሆናል::
[9]እጅህ በጠላቶችህ ላይ በድል አድራጊነት
ከፍ ከፍ ትላለች፤
ጠላቶችህም ሁሉ ይጠፋሉ::

[10]"በዚያን ጊዜ" ይላል *እግዚአብሔር*፤

"ፈረሶቻችሁን ከመካከላችሁ አጠፋለሁ፤
ሠረገሎቻችሁን እደመስሳለሁ::
[11]የምድራችሁን ከተሞች እደመስሳለሁ፤
ምሽጎቻችሁንም ሁሉ አፈርሳለሁ::
[12]ጥንቈላችሁን አጠፋለሁ፤
ከእንግዲህም አታሟርቱም::
[13]የተቀረጹ ምስሎቻችሁን፣
የማምለኪያ ዐምዶቻችሁንም ከመካከላችሁ
አጠፋለሁ፤
ከእንግዲህ ለእጃችሁ ሥራ አትሰግዱም::
[14]የአሼራ ምስል ዐምድ[ከ] ከመካከላችሁ
እነቅላለሁ፤
ከተሞቻችሁንም እደመስሳለሁ::
[15]ያልታዘዙኝን አሕዛብ፣
በቍጣና በመዓት እበቀላቸዋለሁ::"

## የእግዚአብሔር ክስ በእስራኤል ላይ

**6** *እግዚአብሔር* የሚለውን ስሙ፤
"ተነሡ፤ ጕዳያችሁን በተራሮችም፤ ፊት
አቅርቡ፤
ኰረብቶች እናንተ የምትሉትን ይስሙ፤
[2]ተራሮች ሆይ፤ *የእግዚአብሔርን* ክስ
አድምጡ፤
እናንት የምድር ጽኑ መሠረቶችም፤ ስሙ፤
*እግዚአብሔር* ከሕዝቡ ጋር ክርክር አለውና፤
ከእስራኤልም ጋር ይፋረዳል::

*[ቸ]2 ወይም ጎሶች [ኀ]2 ዕብራይስጡ አመጣጡ ይላል ወይም ከዘላለም የሆነ [ነ]2 ወይም ከቀድሞ ቀናት [ፕ]6 ወይም ናምሩድን በመግቢያው በር [ኦ]6 ወይም ያፈርሳሉ [ከ]14 አሼራ የተባለችው አምላክ ትእምርት ነው::*

5፥2 ዘፍ35፥16፤ 48፥7፤ዘኍ24፥19፤ 1ሳሙ13፥4፤ 2ሳሙ6፥21፤ 2ዜና7፥18፤ መዝ102፥25፤ ማቴ2፥6፤ዮሐ7፥42
5፥3 ኤር7፥29
5፥4 ኢሳ40፥11፤ 49፥9፤52፥13፤ ሕዝ34፥11-15፤23፤ ሚክ7፥14፤ሉቃ1፥32
5፥5 ኢሳ8፥7፤ 9፥6፤10፥24-27፤ ሉቃ2፥14፤
5፥6 ዘፍ10፥8፤ ናሆ2፥11-13፤ ሶፎ2፥13
5፥7 መዝ133፥3፤ ኢሳ44፥4፤ አሞ5፥15፤ሚክ2፥12
5፥8 ዘፍ49፥9፤ መዝ50፥22፤ ኢሳ5፥29፤ ሆሴ5፥14፤ሚክ4፥13፤ ዘካ10፥5
5፥9 መዝ10፥12
5፥10 ዘዐ15፥4፡19፤ ሆሴ14፥3፤ ሐጌ2፥22፤ዘካ9፥10
5፥11 ዘዳ29፥23፤ ኢሳ6፥11፤ ሰቆ2፥2፤ሆሴ10፥14፤ አሞ5፥9
5፥12 ዘዳ18፥10-12፤ ኢሳ2፥6፤8፥19
5፥13 ኢሳ2፥18፤ ሕዝ6፥9፤ ሆሴ10፥2፤ናሆ1፥14፤ ዘካ13፥2
5፥14 ዘዐ34፥13፤ መሳ3፥7፤2ነገ17፥10
6፥1 መዝ50፥1፤ ሕዝ6፥2
6፥2 ዘዳ32፥1፤ መዝ50፥7፤ ኢሳ3፥13፤ ኤር2፥9፤ሆሴ12፥2

አውጥተዋል፤ 2ነገ 25፥7 ይመ)::

*5፥2፤* ከቍ 1 አስፈሪ ትንቢት ጋር ሲነጻጸር በዚህ ክፍል ሲነጻጸር ሚክያስ አዎንታዊ ትንቢት ይናገራል:: *ኤፍራታ፤* የቤተ ልሔም ከተማ ያለችበት ግዛት ነው (ሩት 1፥2፡4፥11፣ 1ሳሙ 17፥12 ይመ):: *ገዥ፤* በመጨረሻ ለእግዚአብሔር አብ የሚገዛውን ክርስቶስን ያመለክታል (የ4፥8 ማብ ይመ):: *አመጣጡ ከጥንት፤* በሥጋ ከተወለደበት ዘመን አስቀድሞ ማለት ነው (ዮሐ 8፥58 ይመ):: *ከቀድሞ ዘመን፤* በታሪክም ውስጥ ሆነ (ከ2ሳሙ 7፥12-16፣ ከኢሳ9፥6-7፣ ከአሞ9፥11 ጋር ያነጻጽሩ) ከዘላለም በፊት እንኳ ለማ ለት ነው (አማራጭ ትርጕሙን ይመ)::

5፥3 *እስራኤል ትተዋለች፤* መሲሕ ተወልዶ ገዥ እስከ ሚሆንበት ጊዜ ድረስ ማለት ነው:: *እስራኤል፤* የ1፥5 ማብ ይመ::

5፥4 *ኀይል...ታላቅነት፤* በእግዚአብሔር አብ ብርታትና ግርማ መሲሑ እረኛ ይሆናል፤ ይገዛልም::

5፥5 *ሰላማቸው፤* ኢየሱስ "ሰላማችን" ነው (ኤፌ 2፥14)፤ ከጦርነት ነጻ ከመሆን በተጨማሪ፣ በዕብራይስጥ "ሰላም" የሚለው ቃል ትርጕም በብሉይ ኪዳን ብልጥግናን ያመለክታል፤ "የሰላም ልዑል" የሚለውን የኢሳ 9፥6 ማብ፣ ሉቃ 2፥14 ይመ:: *አሦራዊ፤* በየዘመኑ የሚነሡትን የእግዚአብሔርን ሕዝብ ጠላቶች ሁሉ የሚያሳይ ትእምርት ነው፤ ኢሳ 11፥11፣ ዘካ 10፥10-11 ይመ:: *እናስነሣበታለን፤* (እኛ)፤ የእግዚአብሔርን ሕዝብ ያስነሣበታል ማለት ነው:: *ሰባት...ስምንት፤* ብዛትን ለመግለጽ የገባ ምሳሌያዊ አባባል ነው (የኢዮ 5፥19 ማብ ይመ)::

5፥6 *የናምሩድን ምድር፤* አሦርን ለማለት ነው፤ ዘፍ 10፥8-11 ይመ:: *እርሱ፤* በቍ 2 ላይ የተጠቀሰው ገዥ ነው::

5፥8 *አንበሳ፤* እንዳለፈው ዘይቤያዊ አባባል (ቍ 7) የእግዚአብሔር ሕዝብ በጠላቶቻቸው ላይ የማያጠራጥር ድልን እንደ ሚያገኙ የሚያሳይ ሥዕላዊ አገላለጽ ነው (ቍ 9)::

*5፥10-14፤* በመሲሑ ዘመን የእግዚአብሔር ሕዝብ በጦር መሣ ሪያዎች ወይም በአሕዛብ ጣዖቶች አይታመኑም፤ የሕዝቡ ድልና ስኬታማነት የሚወሰነው ምንጊዜም በእርሱ ላይ ባላቸው መታመን ነው::

*6፥1-16፤* ይህ ምዕራፍ የሚያሳየው እግዚአብሔር በእስራ ኤል ላይ ያለውን የሕግ ክስ የሚያቀርብበትን የፍርድ ቤት ሁኔታ ያሳያል:: ከቍ 1-2 እግዚአብሔር ክሱን አድምጠው፣ ከቍ 9-16 ለተዘረዘሩት ክሶች መከላከያ ሐሳባቸውን እንዲያዘጋጁ ሕዝቡን ይጠ ራቸዋል:: በቍ 3-5 እግዚአብሔር ያደረገላቸውን ቸርነት በሐዘን ሆኖ እያስታወሳቸው ይናገራል:: ከቍ 6-7 እስራኤል ትናገራለች፤ በቍ 8 ደግሞ ሚክያስ በቀጥታ ለሕዝቡ ከቍ 6-7 ለተነሡት ጥያቄ ዎች መልስ ይሰጣል:: በቍ 9-16 እግዚአብሔር ሕዝቡን ተለይተው በሚታወቁ ክፉ ሥራዎቻቸው ይከሳቸዋል::

6፥1-2 *ተራሮች...የምድር ጽኑ መሠረቶችም፤* ግዑዝ የሆኑ ፍጥረታት ለዘመናት ከመኖራቸው የተነሣና የቃል ኪዳኑም ምስክር በመሆናቸው ሦስተኛ ወገን ምስክር ሆነው ተጠርተዋል (ዘዳ 32፥1፤ ኢሱ 24፥27 ይመ፤ ኢሳ 1፥2 እና ማብ ይመ)::

[3]"ሕዝቤ ሆይ፤ ምን አደርጌሃለሁ?
ሸክም የሆንሁብህስ እንዴት ነው?
እስቲ መልስልኝ!
[4]ከግብፅ አወጣሁህ፤
ከባርነት ምድርም ተቤዠሁህ፤
እንዲመሩህ ሙሴን፣
አሮንንና ማርያምን ላክሁልህ::
[5]ሕዝቤ ሆይ፤
የሞዓብ ንጉሥ ባላቅ የመከረውን፣
የቢዖር ልጅ በለዓም የመለሰለትንም እስቲ
አስቡ፤
*የእግዚአብሔርን የጽድቅ ሥራ ታውቁ ዘንድ*፣
ከሰጢም እስከ ጌልገላ የተጓዛችሁትን
አስቡ::
[6]ምን ይዤ *በእግዚአብሔር* ፊት ልቅረብ፣
በልዑል አምላክ ፊት ልስገድ?
የሚቃጠለውን መሥዋዕት፣
ከአንድ ዓመት ጥጃ ጋር ይዤ በፊቱ
ልቅረብን?
[7]በአንድ ሺህ አውራ በጎች፣
በዐሥር ሺህ የዘይት ፈሳሽ *እግዚአብሔር*
ደስ ይለዋልን?
ስለ በደሌ የበኵር ልጄን፣
ስለ ነፍሴም ኀጢአት የሆዴን ፍሬ ላቅርብ
ብለትን?
[8]ሰው ሆይ፤ መልካም የሆነውን አሳይቶሃል፤
*እግዚአብሔር* ከአንተ የሚፈልገው
ምንድን ነው?
ፍትሕን ታደርግ ዘንድ፣ ምሕረትንም
ትወድድ ዘንድ፣
በአምላክህም ፊት በትሕትና ትራመድ
ዘንድ አይደለምን?

## የእስራኤል በደልና ቅጣት

[9]ስምህን መፍራት ጥበብ ነው፤
ስሙ! *እግዚአብሔር* ከተማዪቱን እንዲህ
እያለ ይጣራል፤
"በትሩን አስቡ፤ ያዘጋጀውም ማን እንደ
ሆነ አስታውሱ[n]::
[10]የክፋት ቤት ሆይ፤
በግፍ የተገኘ ሀብታችሁን፣
በሐሰተኛ መስፈሪያ የሰበሰባችሁትን
አስጸያፊ ነገር እረሳዋለሁን?
[11]ዐባይ ሚዛን፣ የያዘውን ሰው፣
ሐሰተኛ መመዘኛ በከረጢት የቋጠረውን
ንጹሕ ላድርገውን?
[12]ባለጠጎቿ ግፈኞች፣
ሰዎቿ ሐሰተኞች ናቸው፤
ምላሳቸውም አታላይ ናት::
[13]ስለዚህ አንተን አጠፋሃለሁ፣
ከኀጢአትህ የተነሣ አፈራርስሃለሁ::
[14]ትበላለህ፤ ነገር ግን አትጠግብም፤
ሆድህ እንዳለ ባዶውን[■] ይቀራል፤
ታከማቻለህ፤ ነገር ግን አይጠራቀምልህም፤
የሰበሰብኸውን ለሰይፍ አደርገዋለሁና::
[15]ትዘራለህ፤ ነገር ግን አታጭድም፤
የወይራ ዘይት ትጨምቃለህ፤ ነገር ግን
ዘይቱን አትቀባም፤
ወይንን ትቈርጣለህ፤ ነገር ግን የወይን ጠጅ
አትጠጣም::
[16]የ*የምሪን ሥርዐት*፣
የአክዓብን ቤት ልምድ ሁሉ የሙጥኝ
ብለሃል፤
ትውፊታቸውንም ተከትለሃል::
ስለዚህ አንተን ለውድመት፣
ሕዝብህን ለመዘባበቻ አሳልፌ እሰጣለሁ፤
አሕዛብም ይሣለቁብሃል[o]::"

## የእስራኤል መከራ

**7** ለእኔ ወዮልኝ!
የወይን ዕርሻ በሚቃረምበት ጊዜ
የበጋ ፍራፍሬ እንደሚለቀም ሰው
ሆኛለሁ፤
የሚበላ የወይን ዘለላ የለም፤
የምንጓጓለት፣ ቶሎ የሚደርሰው በለስም
አልተገኘም::
[2]ፈሪሀ እግዚአብሔር ያደረበት ሰው ከምድር
ጠፍቶአል፤
አንድም እንኳ ቅን ሰው የለም፣
ሰው ሁሉ ደም ለማፍሰስ ያደባል፤
እያንዳንዱም ወንድሙን በመረብ
ያጠምዳል::
[3]እጆቹ ክፉ ለማድረግ ሠልጥነዋል፤
ገዥ እጅ መንሻ ይፈልጋል፤
ፈራጁ ጉቦ ይቀበላል፤
ኀይለኞች ያሻቸውን ያስፈጽማሉ፤
ሁሉም አንድ ላይ ያሤራሉ::

6፥3 ኤር2፥5
6፥4 ዘፀ3፥10፤ 4፥16፤6፥6፤15፥20፤ ዘኍ33፥1፤ዘዳ7፥8፤ መዝ77፥20
6፥5 ዘኍ22፥2፤ 25፥1፤ዘዳ11፥30፤ ኢሱ5፥9-10፤ መሳ5፥11፤1ሳሙ12፥7
6፥6 መዝ40፥6-8፤51፥16-17፤95፥2
6፥7 ዘሌ18፥21፤ 2ነገ3፥27፤መዝ50፥8-10፤ ኢሳ1፥11፤40፥16፤ ሆሴ5፥6፤አሞ5፥22
6፥8 ዘፍ5፥22፤ ዘዳ10፥12-13፤ 1ሳሙ15፥22፤ 2ነገ22፥19፤ ኢሳ1፥17፤ 57፥15፤ኤር22፥3፤ ሆሴ6፥6፤ዘካ7፥9-10፤ ማቴ9፥13፤23፥23፤ ማር12፥33፤ሉቃ11፥42
6፥9 ዘፍ17፥1፤ ኢሳ11፥4
6፥10 ሕዝ45፥9-10፤ አሞ3፥10፤8፥4-6
6፥11 ዘሌ19፥36፤ ዘዳ25፥13
6፥12 መዝ35፥20፤ 116፥11፤ኢሳ1፥23፤ 3፥8፤ኤር9፥3
6፥13 ኢሳ1፥17፤ 6፥11
6፥14 ኢሳ9፥20፤ 30፥6፤ሆሴ4፥10
6፥15 ዘዳ28፥38፤ ኢዮ24፥11፤ ኤር12፥13፤አሞ5፥11፤ ሶፎ1፥13
6፥16 ዘዳ28፥37፤ 1ነገ16፥25፡29፡33፤ ኤር7፥24፤25፥9፤51፥51፤ ሚክ2፥6
7፥1 መሐ2፥13
7፥2 መዝ10፥8፤ 12፥1፤ምሳ6፥17፤ ኢሳ3፥5፤ኤር2፥29፤ 5፥26፤ 8፥6፤ሚክ3፥10
7፥3 ዘፀ23፥8፤ ምሳ4፥16፤ሕዝ22፥12

[n]9 የዚህ ስንኝ የዕብራይስጡ ትርጒም በእርግጠኝነት አይታወቅም:: [■]14 የዚህ ቃል የዕብራይስጡ ትርጒም በእርግጠኝነት አይታወቅም:: [o]16 የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም ከዚህ ጋር ሲስማማ የዕብራይስጡ ግን 'የሕዝቤን ስድብ ትሸከማለህ' ይላል

6፥2 *ከእስራኤልም*፤ እዚህ ላይ በዋነኛነት የሚያመለክተው ይሁዳን ነው::

6፥3 *ሕዝቤ*፤ የርኅራኄ ተግሣጽን ያመለክታል (እንዲሁም ቍ5 ይመ)::

6፥5 *ባላቅ...በለዓም*፤ ዘኍ 22-24 ይመ:: *ከሰጢም እስከ ጌልገላ*፤ ኢሱ 3፥1፤4፥19 ይመ::

6፥6፤ ተመሳሳይ የሆነ ሐሳብ በ1ሳሙ 15፥22፤ መዝ 51፥16፤ ሆሴ 6፥6፤ ኢሳ 1፥11-15 (የዚሁኑ ማብ ይመ) ተገልጾአል:: ሚክያስ መሥዋዕት አስፈላጊ መሆኑን አልካደም፤ ነገር ግን መሥዋዕት ከመታዘዝ ውጭ ሆኖ ቢቀርብ ዋጋ እንደሌለው ያሳያል::

6፥8 *ሰው*፤ ሚክያስ ለእስራኤል ሁሉ የሚናገር ቢሆንም እንኳ በነጠላ ቍጥር ክሱ ቀረበ፣ ለግል መሆኑን ያመለክታል (ዘዳ 10፥12-13 ይመ):: *ፍትሕን ታደርግ ዘንድ፣ ምሕረትንም ትወድድ ዘንድ*፤ እግዚአብሔር ከቃል ኪዳኑ ሕዝብ የሚጠብቀው የመታዘዝ ዐይነት ነው::

6፥9 *ከተማዪቱን*፤ ኢየሩሳሌምን ነው::

6፥11፤ ምሳ 11፥1፡20፥23፤ ሆሴ 12፥7፤ አሞ 8፥5 ይመ::

6፥12 *ሰዎቿ (የእርስዋ)*፤ የኢየሩሳሌም ለማለት ነው::

6፥13 *ስለዚህ*፤ የ2፥3 ማብ ይመ::

6፥16 *የዖምሪን...የአክዓብን*፤ በ1ነገ 16፥25፡30 ከእነርሱ በፊት ከነበሩት ነገሥታት የባሰ ክፋት እንደፈጸሙ ያመለክታል::

*7፥1-20*፤ በዚህ ምዕራፍ የተጠቀሱት ተናጋሪዎች ሚክያስ (ቍ1-7)፣ ጽዮን (ቍ 8-10)፣ ሚክያስ (ቍ 11-13)፣ ጽዮን (ቍ 14)፣ እግዚአብሔር (ቍ 15)፣ ሚክያስ (ቍ 16-20) ናቸው:: ምዕራፉ ጨለምለም ባለ ሐሳብ ቢጀምርም፣ ተስፋ ሰጭ በሆነ ዐረፍተ ነገር ይደመድማል::

*7፥1-2*፤ ጻድቅን ሰው ፈልጎ ማግኘት የመከር ወቅት ካለፈ በኋላ የበጋን ፍሬ እንደ መፈለግ ነው፤ እንዲሁም (ኤር 8፥20 ይመ):: የሚሸበሩበትም ጊዜ፤

[4]ከእነርሱ ይሻላል የተባለው እንደ አሜከላ፣
 እጅግ ቀና የተባለውም እንደ ኵርንችት
 ነው፤
የጠባቂዎቻችሁ ቀን ደርሶአል፤
 የእግዚአብሔር የፍርድ ቀን መጥቶአል፤
የሚሸበሩበትም ጊዜ አሁን ደርሶአል።
[5]ባልንጀራህን አትመን፤
 በጓደኛህም አትታመን፤
በዕቅፍህ ለምትተኛዋ እንኳ፣
 ስለምትነግራት ቃል ተጠንቀቅ።
[6]ወንድ ልጅ አባቱን ይንቃል፤
 ሴት ልጅ በእናቷ ላይ፤
ምራት በአማቷ ላይ ትነሣለች፤
 የሰው ጠላቶች የገዛ ቤተ ሰዎቹ ናቸውና።

[7]እኔ ግን እግዚአብሔርን ተስፋ አደርጋለሁ፤
 አዳኜ የሆነውን አምላክ እጠብቃለሁ፤
አምላኬ ይሰማኛል።

## እስራኤል ትነሣለች

[8]ጠላቴ ሆይ፤ በእኔ ላይ በደረሰው ደስ
 አይበልሽ!
 ብወድቅም እንኳ እነሣለሁ፤
በጨለማ ብቀመጥ እንኳ፣
 እግዚአብሔር ብርሃኔ ይሆናል።
[9]እርሱን ስለ በደልሁ፣
 እስኪቆምልኝ
እስኪፈርድልኝም ድረስ፣
 የእግዚአብሔርን ቍጣ እቀበላለሁ፤
እርሱ ወደ ብርሃን ያወጣኛል፤
 እኔም ጽድቁን አያለሁ።
[10]ጠላቴም ታያለች፤
 ኀፍረትንም ትከናነባለች፤
"አምላክህ እግዚአብሔር የት አለ?"
 ያለችኝን፣
ዐይኖቼ ውድቀቷን ያያሉ፤
 አሁንም እንኳ፣
 እንደ መንገድ ጭቃ ትረገጣለች።

[11]ቅጥሮቻችሁን የምትሠሩበት፣
 ድንበራችሁንም የምታሰፉበት ቀን
 ይመጣል።
[12]በዚያ ቀን ሰዎች፣
 ከአሦር እስከ ግብፅ ከተሞች፣
ከግብፅ እስከ ኤፍራጥስ፣
ከባሕር ወደ ባሕር፣
 ከተራራ ወደ ተራራ ወደ እናንተ
 ይመጣሉ።
[13]ከሥራቸው የተነሣ፣
 በነዋሪዎቿ ምክንያት ምድር ባድማ
 ትሆናለች።

## ጸሎትና ውዳሴ

[14]ብቻቸውን በዱር ውስጥ፣
 በለመለመ መስክ* የሚኖሩትን፣
የርስትህ መንጋ የሆኑትን፣
 ሕዝብህን በበትርህ ጠብቅ፤
እንደ ቀድሞው ዘመን፣
 በባሳንና በገለዓድ ይሰማሩ።

[15]"ከግብፅ እንደ ወጣህበት ዘመን ሁሉ፣
 ታምራቴን አሳያቸዋለሁ።"

[16]አሕዛብ ያያሉ፣ ያፍራሉም፤
 ኀይላቸውን ሁሉ ያጣሉ፤
አፋቸውን በእጃቸው ይይዛሉ፤
 ጆሮአቸውም ትደነቍራለች።
[17]በደረታቸው እንደሚሳቡ ፍጥረታት፣
 እንደ እባብም ትቢያ ይልሳሉ፤
ከዋሻቸው እየተንቀጠቀጡ ይወጣሉ፤
 በፍርሀትም ወደ አምላካችን ወደ
 እግዚአብሔር ይመለሳሉ፤
እናንተንም ይፈራሉ።
[18]የርስቱን ትሩፍ፣
 ኀጢአት ይቅር የሚል፣ የሚምር
እንደ አንተ ያለ አምላክ ማነው?
 ለዘላለም አትቈጣም፤
ነገር ግን ምሕረት በማድረግ ደስ ይልሃል።
[19]ተመልሰህ ትራራልናለህ፤
 ኀጢአታችንን በእግርህ ትረግጣለህ፤
በደላችንንም ሁሉ ወደ ጥልቁ ባሕር
 ትጥላለህ።
[20]ከቀድሞ ዘመን ጀምሮ
 ለአባቶቻችን በመሐላ ቃል እንደ
 ገባህላቸው፣
ለያዕቆብ ታማኝነትን፣
 ለአብርሃምም ምሕረትን ታደርጋለህ።

7፥4 ዘኍ33፥55፤ 2ሳሙ23፥6፤ ኢዮ31፥14፤ ኢሳ22፥5፤ ሕዝ2፥6፤ሆሴ9፥7
7፥5 ኤር9፥4
7፥6 ሕዝ22፥7፤ ማቴ10፥35-36፤ ማር13፥12
7፥7 መዝ4፥3፤ 130፥5፤ኢሳ21፥8፤ 25፥9
7፥8 2ሳሙ22፥29፤ መዝ20፥8፤22፥17፤ 37፥24፤ምሳ24፥17፤ ኢሳ9፥2፤አሞ9፥11፤ ሚክ4፥11
7፥9 መዝ107፥10፤ 119፥154፤ ኢሳ46፥13፤ ሰቆ3፥39-40
7፥10 ሳሙ22፥43፤ ኢዮ40፥12፤ መዝ35፥26፤42፥3፤ ኢሳ5፥5፤51፥23፤ ዘካ10፥5
7፥11 ኢሳ54፥11፤ አሞ9፥11
7፥12 ኢሳ11፥11፤ 19፥23-25፤60፥4
7፥13 ኢሳ3፥10-1፤ ሕዝ12፥19፤33፥28-29
7፥14 መዝ23፥4፤ 28፥9፤95፥7፤ መሐ4፥1፤ኢሳ33፥9፤ ኤር50፥19፤ ሕዝ36፥11፤ሚክ5፥4
7፥15 ዘፀ3፥20፤ መዝ78፥12
7፥16 መሳ18፥19፤ ኢሳ26፥11
7፥17 ዘፍ3፥14፤ 2ሳሙ22፥46፤ ኢሳ25፥3፤59፥19
7፥18 ዘፀ8፥10፤ 34፥9፤1ሳሙ2፥2፤ 2ዜና6፥21፤30፥9፤ መዝ103፥8-13 ኢሳ43፥25፤54፥9፤ ኤር31፥20፤32፥41፤ 50፥20፤ሕዝ18፥23፤ ኢል2፥32፤ አሞ5፥15፤ሚክ2፥12፤ ዘካ3፥4
7፥19 ኢሳ43፥25፤ ኤር31፥34 ሉቃ1፥72
7፥20 ዘዳ7፥8፤ መዝ108፥4፤ገላ3፥16፤

*14 ወይም 'በቀርሜሎስ መካከል'

7፥4 *የጠባቂዎቻችሁ ቀን*፤ ነቢያት ማስጠንቀቂያ የሰጡበትን የፍርድን ቀን ያመለክታል (ኤር 6፥17፤ ሕዝ 3፥17-21 ይመ)። የሚሸበሩበትም ጊዜ፤

*7፥6*፤ የቤተ ሰቡ መሠረት በመፈራረስ ላይ ነበር።

7፥8፤ *በእኔ፤* ጽዮን ናት። *ጠላቴ ሆይ*፤ ሌሎችን ሕዝቦች ማለት ነው። *ብወድቅም እንኳ*፤ ሚክያስ ጽዮን በ586 ዓ.ቅ.ክ. እንደምትደመሰስ አስቀድሞ አየ።

7፥14 *የርስትህ* እስራኤልን ነው (ቍ 18፤ መዝ 94፥14 ይመ)።

*7፥15-17*፤ እነዚህ ጥቅሶች እግዚአብሔር በዘፀአት እንዳደረገው ሁሉ አሕዛብ አይተውና ዐፍረው በፍርሀት ወደ ጌታ ይመለሱ ዘንድ ድንቁን እንደገና እንደሚያሳይ የሚያመለክት ጸሎት ይዘዋል ማለት ይቻላል።

*7፥16*፤ አሕዛብ በመሲሑ መምጣት የእግዚአብሔርን ኀይል ሲያዩ፣ እጅግ ይደነቃሉ።

7፥17፤ *እንደ እባብም ትቢያ ይልሳሉ*፤ ሽንፈትን የሚያመለክት ሥዕላዊ አገላለጽ ነው።

*7፥18-20*፤ የምዕራፍ 7 ብቻ ሳይሆን፣ የመጽሐፉ ማጠቃለያ ነው።

7፥18 *እንደ አንተ ያለ አምላክ ማነው?* የሚክያስን ስም በሌላ መልኩ የሚገልጽ የቃላት ጨዋታ ነው። (የ1፥1 ማብ ይመ)፤ ከዘፀ 15፥11፤ መዝ 89፥6 ጋር ያነጻጽሩ)።

7፥19 *በደላችንንም ሁሉ ወደ ጥልቁ ባሕር*፤ የኢሳ 38፥17 ማብ ይመ።

7፥20 *ለያዕቆብ...ለአብርሃምም*፤ እግዚአብሔር ለአብርሃምና (ዘፍ 22፥17) ለያዕቆብ (ዘፍ 28፥14) ዘራቸው እንደ ምድር ዐፈርና እንደ ባሕር ዳር አሸዋ እንደሚበዛ፤ ቃል ገብቶላቸዋል፤ እንዲሁም አብርሃም የብዙዎች አሕዛብ አባት እንደሚሆን ቃል ገብቶለታል (ዘፍ 17፥5 ይመ፤ ከሉቃ 1፥54-55 ጋር ያነጻጽሩ)። አማኞች ሁሉ የዚህ ተስፋ ወራሾች ናቸው (ሮሜ 4፤ ገላ 3፥6-29፤ ዕብ 11፥12)።

# ትንቢተ ናሆም

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ይህ መጽሐፍ ናሆም ያየውን ራእይ የያዘ ነው (1፥1)፤ ናሆም የስሙ ትርጉም "መጽናናት" ማለት ሲሆን፣ "እግዚአብሔር ያጽናናል" ወይም "የእግዚአብሔር ማጽናናት" የሚል ትርጉም ካለው ከነህምያ ስም ጋር ይመሳሰላል:: የናሆም መጽሐፍ መሪ ሐሳብ የሆነው የነነዌ ውድቀት፣ ለይሁዳ መጽናናትን የሚያመጣ ነው:: የተወለደበት ከተማ ኤልቆሽ ከመሆኑ በስተቀር ስለ ናሆምም ሆነ ስለተወለደበት ስፍራ ብዙ የሚታወቅ ነገር የለም::

### የተጻፈበት ጊዜ

ጸሐፊው በ663 ዓ.ቅ.ክ የተፈጸመው የኖእ አሞን ውድቀት ያለፈ መሆኑን ይናገራል (3፥8-10):: ናሆም በሦስቱም የመጽሐፉ ምዕራፎች ውስጥ የተነበየው በ612 ስለ ተፈጸመው ስለ ነነዌ ውድቀት ስለ ሆነ ትንቢቱ የተነገረው በ663 እና በ612 ዓ.ቅ.ክ ባለው ጊዜ ውስጥ ሊሆን ይችላል:: ነቢዩ በዚሁ መጽሐፉ የነነዌ ውድቀት በደጅ እንደ ሆነ ስለሚናገር (2፥1፤ 3፥14:19)፣ ጊዜው ምናልባት ወደ ምእተ ዓመቱ ማብቂያ ገደማ ሳይሆን አይቀርም:: በዚህ መሠረት ናሆም የኖረው በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት፣ ሶፎንያስና ወጣቱ ኤርምያስ በነበሩበት ጊዜ እንደሆነ መገመት ይቻላል::

### ታሪካዊ ዳራው

በም 1፥1 ላይ ነነዌ ተብላ የተጠቀሰችው አሦር፣ በ722-721 ዓ.ቅ.ክ ሰማርያን ስለአጠፋች በእስራኤል ሰሜናዊ ግዛት የነበረው ሕዝብ በምርኮ ተወስዶአል፤ በይሁዳ ላይ ከፍተኛ ስጋት የምትፈጥር ሆና ነበር:: አሦራውያን እጅግ ጨካኞች ነበሩ፤ ንጉሦቻቸው ሁልጊዜ በተሸነፉ ሕዝቦች ላይ በሚፈጸሙ አሠቃቂ ቅጣት ይደሰቱ ነበር:: በውጊያ የሚሸነፉትን ሕዝብ ከአገሩ አፈናቅለው ወደ ሌሎች ግዛቶቻቸው በማጋዝ አረመኔያዊ ተግባር በላያቸው መፈጸም የመንግሥት መመሪያቸው ነበር:: የተሸነፉ ከተሞች መሪዎች ከመገደላቸው በፊት፣ እንዲሠቃዩና ዘግናኝ በሆነ ሁኔታ አካላቸው እንዲቈራረጥ ይደረግ ነበር:: (የ3፥3 ማብ ይመ)::

ንጉሥ ሰናክሬም በ700 በዓ.ቅ.ክ፣ ነነዌ የአሦር ግዛት ዋና ከተማ እንድትሆን አደረገ፤ በ612 እስከጠፋችበት ጊዜ ድረስ ዋና ከተማ እንደሆነች ቈይታለች:: ቀደም ሲል ከተማዋ እንደምትጠፋ ዮናስ አስታውቆ ነበር (ዮና 3፥4)፤ ነገር ግን ሕዝቡ ንስሓ በመግባቱ፣ ሊደርስባት የነበረው ጥፋት ለጊዜው ቀርቶአል:: በኋላ ግን ነነዌ ብዙም ሳትቈይ ከቀድሞው በባሰ ሁኔታ ወደ ክፋቷ፣ ወደ ጭከናዋና ወደ ትዕቢቷ ተመለሰች:: በታላቁ የአሦር መሪ በአሰናፈር ዘመነ መንግሥት (669-627) ክፋቷ ከፍተኛ ደረጃ ላይ ደረሰ:: ንጉሡ ከሞተ በኋላም ነነዌ እስከ ወደቀችበት (612) ድረስ አሦር የነበራት ኀይልና ዝና እያሽቈለቈለ መጣ (የ1፥14፤2፥1 ማብ ይመ)::

### የመጽሐፉ ተደራስያን

በመጽሐፉ ውስጥ የተጠቀሱት አንዳንድ ቃላት ይሁዳን የሚመለከት ሲሆን (1፥12-13:15 ይመ)፣ አብዛኛው ግን ለነነዌ (1፥11:14፤2፥1:13፤ 3፥5-17:19) ወይም ለንጉሥዋ (3፥18) የተጻፈ ነው:: ይሁን እንጂ መጽሐፉን የሚያነቡት የይሁዳ ሰዎች ነበሩ::

### ሥነ ጽሑፋዊ ዘዬው

የጽሑፉ ይዘት በፍርድ ላይ አጽንዖት የሚያደርግ ሲሆን፣ ለዚህም ትክክለኛ አገላለጽና ምርጥ ቃላት እንደዚሁም ጥልቅ ስሜት፣ ጠንካራ እይታና ድምፀት ተጠቅሞአል:: ቋንቋው ቅኔያዊ ሲሆን፣ ብዙ ተለዋዋጭና ተነጻጻሪ ዘይቤዎችን፣ ሥዕላዊ ቃላትን፣ የመደጋገም ሥልትንና በርካታ አጫጭር ሐረጎችን ያካተተ ነው::

### ከትምህርተ መለኮት አንጻር ያሉ መሪ ሐሳቦች

የመጽሐፉ ማእከላዊ ሐሳብ በነነዌ ላይ ስለሚፈጸመው የእግዚአብሔር ፍርድ ሲሆን፣ ይህም ግፍና ጭካኔ፣ ክፋትና ጣዖትን ማምለክ ከተሞላበት አድራጐቷ የተነሣ ነው፤ መልእክቱም የሚደመደመው በከተማዋ መጥፋት ነው::

በሮሜ 11፥22 ላይ እንደተጠቀሰው እግዚአብሔር ቸር ብቻ ሳይሆን ጨካኝም ነው:: በትንቢተ ናሆም መጽሐፍ መሠረት እግዚአብሔር ለቍጣ የዘገየና (1፥3) ለሚታመኑበት መሸሸጊያ ብቻ ሳይሆን (1፥7)፣ ኀጢአተኛውን ሳይቀጣ የማይተዉም (1፥3) አምላክ ነው:: በስተ መጨረሻ የእግዚአብሔር ጽድቅና ትክክለኛ መንግሥት አሸናፊ ይሆናል፤ አሦር እንደ ወደቀች ሁሉ በክፋት ላይ የተመሠረተና ጨካኝ መንግሥትም በመጨረሻ መውደቁ የማይቀር ነው:: ከዚህም በተጨማሪ እግዚአብሔር የታሪክና የመንግሥታት ሁሉ ጌታ በፍጥረተ ዓለም ላይ ሉዐላዊ አምላክ መሆኑን ናሆም ይናገራል::

### አስተዋፅኦ

1. ርእስ (1፥1)

2. በነነዌ ላይ የሚፈርደው ዳኛ (1፥2-15)
    ሀ. የእግዚአብሔር ቸርነትና ጭካኔ (1፥2-8)
    ለ. የነነዌ መጣልና የይሁዳ ደስታ (1፥9-15)
3. በነነዌ ላይ የተሰጠው ፍርድ (ም2)
    ሀ. የነነዌ መከበብ (2፥1-10)
    ለ. ነነዌ ባድማ መሆንዋ ቀድሞ ከነበራት ክብር ጋር ሲነጻጸር (2፥11-13)
4. የነነዌ ሙሉ በሙሉ መጥፋት (ም3)
    ሀ. የነነዌ ኀጢአት (3፥1-4)
    ለ. በነነዌ ላይ የደረሰው ጥፋት (3፥5-19)

1 ስለ ነነዌ ጥፋት የተነገረ ንግር፤ የኤልቆሻዊው የናሆም የራእዩ መጽሐፍ ይህ ነው፤

**በነነዌ ላይ የተገለጠ የእግዚአብሔር ቍጣ**

²*እግዚአብሔር* ቀናተኛና ተበቃይ ስምባክ ነው፤
*እግዚአብሔር* የሚበቀል፣ በመዓትም
የተሞላ ነው::
*እግዚአብሔር* ባላጋራዎቹን ይበቀላል፤
በጠላቶቹም ላይ ቍጣውን ያመጣል
³*እግዚአብሔር* ለቍጣ የዘገየ በኀይሉም
ታላቅ ነው፤
*እግዚአብሔር* በደለኛውን ሳይቀጣ አያልፍም፤
መንገዱ በወውሎ ነፋስና በማዕበል ውስጥ ነው፤
ደመናም የእግሩ ትቢያ ነው::
⁴ባሕርን ይገሥጻል፤ ያደርቀዋልም፤
ወንዞችን ሁሉ ያደርቃል::
ባሳንና ቀርሜሎስ ጠውልገዋል፤
የሊባኖስም አበቦች ረግፈዋል::
⁵ተራሮች በፊቱ ታወኩ፤
ኰረብቶችም ቀለጡ::
ምድር በፊቱ፣
ዓለምና በውስጧ የሚኖሩት ሁሉ ተናወጡ::
⁶ቍጣውን ማን ሊቋቋም ይችላል?
ጽኑ ቍጣውንስ ማን ሊሸከም ይችላል?
መዓቱ እንደ እሳት ፈሰሰ፤
ዐለቶችም በፊቱ ተሰነጣጥቀዋል::
⁷*እግዚአብሔር* መልካም ነው፤
በጭንቅ ጊዜም መሸሸጊያ ነው::
ለሚታመኑበት ይጠነቀቅላቸዋል፤
⁸ነነዌን ግን፣
በሚያጥለቀልቅ ጐርፍ ያጠፋታል፤
ጠላቶቹንም ወደ ጨለማ ያሳድዳቸዋል::

1፥1 ዘፍ10፥11፤ኢሳ 1፥1፤13፥1፤19፥1፤ ኤር 23፥33:34፤ 50፥18፤ ናሆ2፥8፤ 3፥7
1፥2 ዘፍ4፥24፤ዘፀ 20፥5፤ዘዳ7፥10፤32፥41፤ መዝ94፥1
1፥3 ዘፀ14፥21፤ 34፥7፤ 2ሳሙ22፥10፤2ነገ2፥1 ፤ነህ9፥17፤መዝ50፥3፤ 104፥3
1፥4 ዘፀ14፥22፤ 2ሳሙ 22፥16፤ኢሳ 33፥9
1፥5 ዘፀ19፥18፤ኢ ዮ9፥6፤ሕዝ38፥20፤ ኢል2፥10፤ሚክ1፥4
1፥6 1ነገ19፥11፤ መዝ76፥7፤130፥3፤ ኢሳ5፥24-25፤ 42፥25፤ኤር10፥10፤ሕ ዝ22፥14
1፥7 መዝ1፥6፤22፥9፤ ኤር17፥17፤33፥11
1፥8 ኢሳ8፥7፤ ዳን9፥26
1፥9 ሆሴ7፥15
1፥10 2ሳሙ23፥6፤ ኢሳ5፥24፤49፥26፤ ሚል4፥1
1፥12 ኢሳ10፥34፤ 54፥6-8፤ሰቆ3፥31-32
1፥13 ኢዮ12፥18፤ መዝ107፥14፤ኢሳ9፥4
1፥14 ኢሳ14፥22፤ ኤር28፥8፤ሕዝ32፥ 22-23፤ሚክ5፥13
1፥15 ዘሌ23፥2-4፤ኢሳ 40፥9፤52፥1:7፤ሐሥ 10፥36፤ሮሜ10፥15

⁹*በእግዚአብሔር* ላይ ምንም ቢያሤሩ[u]፣
እርሱ ያጠፋዋል፤
መከራም ዳግመኛ አይነሣም::
¹⁰በእሾህ ይጠላለፋሉ፤
በወይን ጠጃቸውም ይሰክራሉ፤
እሳትም እንደ ገለባ[^] ይበላቸዋል::
¹¹ነነዌ ሆይ፤ *በእግዚአብሔር* ላይ የሚያሤር፣
ክፋትንም የሚመክር፣
ከአንቺ ዘንድ ወጥቶአል::
¹²*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"ምንም ኀይለኞችና ብዙዎች ቢሆኑም፣
ይቈረጣሉ፤ ይጠፋሉም::
ይሁዳ ሆይ፤ ከዚህ በፊት ባስጨንቅሁም፣
ከእንግዲህ አላስጨንቅሁም::
¹³አሁንም ቀንበራቸውን ከዐንገትህ ላይ
አንሥቼ እሰብራለሁ፤
የታሰርህበትንም ሰንሰለት በጥሼ
እጥላለሁ::"
¹⁴አንቺ ነነዌ፤ *እግዚአብሔር* ስለ አንቺ
እንዲህ ብሎ አዞአል፤
"ስም የሚያስጠራ ትውልድ አይኖራችሁም፤
በአማልክቶቻችሁ ቤት ያሉትን፣
የተቀረጹትን ምስሎችና ቀልጠው
የተሠሩትን ጣዖታት እደመስሳለሁ፤
መቀበሪያህን እምስልሃለሁ፤
አንተ ክፉ ነህና::
¹⁵እነሆ፤ የምሥራች የሚያመጣውን፣
ሰላምን የሚያውጀው ሰው እግር፣
በተራሮች ላይ ነው፤

[u]9 *በእግዚአብሔር ላይ የምታሤሩት ምንድን ነው?* የሚሉ አሉ
[^]10 የዕብራይስጡ ትርጒም በትክክል አይታወቅም::

*1፥1፤* የመጽሐፉ ርእስ የተጠቀሰበት ነው:: *ንግር፤* የኢሳ 13፥1 ማብ ይመ:: *ነነዌ፤* ከመግቢያው "ታሪካዊ ዳራ" የሚለውን ይመ፤ እንዲሁም የዮና 1፥2፤ 3፥3፥ምንብ ይመ፡ በዚህ ላይ ዋናው ከተማ ነነዌ፣ መላውን የአሦርን ግዛት ይወክላል:: *የራእዩ፤* የኢሳ1፥1 ማብ ይመ:: *የኤልቆሻዊው የናሆም፤* ከመግቢያው "ጸሓፊው" የሚለውን ይመ::

*1፥2-3፤* የኪዳኑ ስም የሆነው ያህዌ (*እግዚአብሔር*) በዚህ ስፍራ አጽንዖት ተሰጥቶታል::

1፥2 *ቀናተኛና፤* የዘፀ20፥5 ማብ ይመ:: *ተበቃይ...የሚበቀል...ይበቀላል፤* እግዚአብሔር እርሱንና መንግሥቱን የሚቃወሙትን ሁሉ በጽድቅ ይፈርድባቸዋል:: ተደጋግሞ መጠቀሱ፣ አጽንዖትን እንደተሰጠው የሚያሳይ ነው::

1፥3 *በደለኛውን፤* እንደ ነነዌ ዐይነቱን ማለት ነው:: *በዐውሎ ነፋስና በማዕበል...ደመናም፤* የመዝ 18፥7-15፤ 68፥4፤ 77፥ 16-19፤104፥3-4 ማብ ይመ::

1፥4 *ባሕርን ይገሥጻል፤ ያደርቀዋልም፤* ቀይ ባሕርን በተሻገሩ ጊዜ እንዳደረገው ዐይነት ማለት ነው (ዘፀ14):: *ወንዞችን ሁሉ ያደርቃል፤* ዮርዳኖስን በተሻገሩ ጊዜ እንዳደረገው ዐይነት ነው (ኢሱ3):: *ባሳንና፤* በለም የግጦሽ መሬት የታወቀ ነው (አሞ4፥1):: *ቀርሜሎስ፤* በወይን ዕርሻ የታወቀ ነው(አሞ1፥2):: *የሊባኖስም፤* በምርጥ ዛፎቹ የታወቀ ነው (ሕዝ31፥16):: ማሕ 7፥5፤ የኢሳ 2፥13፤33፥9፤35፥2፤የአሞ4፥1 ማብ ይመ:: ይሁን እንጂ እነዚህ ሁሉ በእግዚአብሔር ቃል ይደርቃሉ::

1፥5 *ተራሮች...ኰረብቶችም...ምድር...ዓለምና፤* የጽናትና የቋሚ ነገር ምልክቶች ናቸው::

1፥6 *ማን ሊቋቋም ይችላል?...ማን ሊሸከም ይችላል?* መልስ ዐዘል ጥያቄዎች ናቸው:: ተራሮች በእግዚአብሔር ፊት ሲንቀጠቀጡ (ቍ5) አልጐዳም ብሎ የሚያስብ የሰው ልጅ ማን ነው?፤ ከሮሜ2፥3-5 ጋር ያነጻጽሩ::

1፥7 *ለሚታመኑበት፤* እንደ ይሁዳ ለማለት ነው::

1፥8 *በሚያጥለቀልቅ ጐርፍ፤* ወራሪውን ኀይል በትእምርት የሚገልጽ ነው (ኢሳ8፥7-8 ይመ):: *ያጠፋታል...ጨለማ፤* በ612 ዓ.ቅ.ክ. ያ ጥፋት በነነዌ ላይ ደረሰ፤ ጨለማም ዋጣት:: በዮናስ አገልግሎት አማካይነት ነነዌ ቀደም ሲል የእግዚአብሔርን ብርሃን አግኝታ ነበር ኋላ ግን ገፋችው፤ ውጤቱም የጨለማን ፍርድ አስከተለ::

1፥9 *ቢያሤሩ፤* የቍ11 ማብ ይመ:: *መከራም ዳግመኛ አይነሣም፤* እግዚአብሔር አሦራውያን በአይሁዳውያን ላይ ለሁለተኛ ጊዜ ድል እንዲያገኙ አልፈቀደላቸውም፤ የመጀመሪያው የሰሜኑ መንግሥት የሰማርያ መውደቅ ነበር (722-721 ዓ.ቅ.ክ.)፤ ሰናክሬም በ701 ያደረገው ወረራ ፍጹም ድልን አላስገኘም (2ነገ18፥13-19፥37፤ኢሳ 36-37 ይመ)::

1፥10 *በወይን ጠጃቸውም ይሰክራሉ፤* 3፥11 እና ማብ ይመ::

1፥11 *የሚያሤር፤* ምናልባት የመጨረሻው የአሦር ታላቁ ንጉሡ ነገሥትና በምዕራብ በኩል ዘምቶ ግብፅን የገዛውና ንጉሥ ምናሴም እንዲገብርለት ያደረገው የአሦር ንጉሥ አሹር ባኒፓል ሳይሆን አይቀርም(ከ669-627 ዓ.ቅ.ክ.)፤ 2ዜና33፥11-13 ይመ::

1፥12 ቢሆኑም (እነርሱ)፤ አሦራውያንን ማለት ነው:: *ባስጨንቅሁም፤* እግዚአብሔር በአካዝ ዘመን (ኢሳ10፥5)እንደገናም በምናሴ ዘመን፣ ቃል ኪዳኑን ያፈረሰውን ሕዝብ ለመቅጣት አሦራውያንን የቍጣው በትር አድርጎ ተጠቅሞባቸዋል::

1፥13 *ቀንበራቸውን...እሰብራለሁ፤* ይሁዳ የአሦር ገባር ሆና ነበር፣ ስለዚህ ያ ቀንበር ይሰበራል::

1፥14 *መቀበሪያህን እምስልሃለሁ፤* እግዚአብሔር ባቢሎናውያንን፣ ሜዶናውያንንና ስካይትያንስን የነነዌን መቃብር እንዲቈፍሩ በ612 ዓ.ቅ.ክ. ተጠቅሞባቸዋል፤ የዚህን ትንቢት ፍጻሜ በተመለከተ ሕዝ32፥22-23 ይመ::

1፥15 *በተራሮች፤* የይሁዳና የኢየሩሳሌም ናቸው:: *የምሥራች የሚያመጣውን.. ሰው እግር፤* ይህ ጥቅስ ትድግናን በሚያሳዩ ብዙ ዐውዶች ውስጥ ተግባራዊ የሚሆን መርሕን ያመለክታል:: በዚህ ስፍራ የተገለጸው ትድግና ግን ከአሦራውያን

ይሁዳ ሆይ፤ በዓላትህን አክብር፤
ስእለትህንም ፈጽም፤
ከእንግዲህ ክፉዎች አይወሩህም፤
እነርሱም ፈጽመው ይጠፋሉ::

**የነነዌ አወዳደቅ**

**2** ነነዌ ሆይ፤ አጥቂ መጥቶብሻል፤
ምሽግሽን ጠብቂ፤
መንገድሽን ሰልዪ፤
ወገብሽን ታጠቂ፤
ኀይልሽን ሁሉ አሰባስቢ::

[2]አጥፊዎች ባድማ ቢያደርጓቸውም፣
የወይን ተክል ቦታቸውን
ቢያጠፉባቸውም፣
እንደ እስራኤል ክብር ሁሉ፣
እግዚአብሔር የያዕቆብንም ክብር
ይመልሳል::

[3]የወታደሮቹ ጋሻ ቀይ ነው፤
ተዋጊዎቹ ቀይ ልብስ ለብሰዋል፤
ዝግጁ በሆኑበት ቀን፣
የሠረገሎቹ ብረት ያብረቀርቃል፤
የጦሩ ዘንግ ይወዛወዛል::
[4]ሠረገሎች በአደባባይ ወዲያ ወዲህ
ይከንፋሉ፤
በመንገዶችም ላይ ይርመሰመሳሉ፤
የሚንበለበል ፋና ይመስላሉ፤
እንደ መብረቅም ይወረወራሉ::

[5]ምርጥ ተዋጊዎቹን ይጠራል፤
ዳሩ ግን መንገድ ላይ ይሰናከላሉ፤
ወደ ከተማዪቱ ቅጥር ይሮጣሉ፤
መከላከያ ጋሻውም በቦታው አለ::
[6]የወንዙ በር ወለል ብሎ ተከፈተ፤
ቤተ መንግሥቱም ወደቀ::
[7]ከተማዪቱ መማረኳና መወሰዷ እንደ
ማይቀር፣
አስቀድሞ ተነግሮአል[ለ]፤
ሴቶች ባሪያዎቿ እንደ ርግብ ያለቅሳሉ፤
ደረታቸውንም ይደቃሉ::
[8]ነነዌ እንደ ኵሬ ናት፤
ውሃዋም ይደርቃል፤
"ቁም! ቁም!" ብለው ይጮኻሉ፤
ነገር ግን ወደ ኋላ የሚመለስ የለም::
[9]ብሩን ዝረፉ፤
ወርቁን ንጠቁ፤
በየግምጃ ቤቱ ያለው፤
የተከማቸውም ሀብት ስፍር ቍጥር
የለውም::
[10]ተበዝብዛለች፤ ተዘርፋለች፤ ተራቍታለች::
ልብ ቀልጦአል፤ ጕልበት ተብረክርኮአል፤
ሰውነት ተንቀጥቅጦአል፤ ፊት ሁሉ
ገርጥቶአል::

[11]አሁን ታዲያ የአንበሶቹ ዋሻ፣
ደቦሎቻቸውን ያበሉበት
ወንዱና ሴቷ አንበሳ የሄዱበት፣
ግልገሎችም ሳይፈሩ የተሰማሩበት ቦታ
ወዴት ነው?

2፥1 ኢር51፥20
2፥2 ኢሳ60፥15፤ ሕዝ 37፥23
2፥3 ሕዝ23፥14-15
2፥4 ኢር4፥13፤ሕዝ 23፥24
2፥5 ኢር46፥12
2፥6 ኢሳ45፥1፤ ናሆ3፥13
2፥7 ዘፍ8፥8፤ኢሳ 32፥12፤59፥11
2፥10 ኢሱ2፥11፤ 7፥5፤ኢሳ29፥22
2፥11 ኢሳ5፥29

[ሀ]3 የዕብራይስጡ ትርጕም ከዚህ ጋር ይስማማል፤ የሰብዓ ሊቃናቱና የሱርስቱ ቅጆች ግን ፈረሰኞች ይፈጥናሉ ይላሉ::
[ለ]7 የዕብራይስጡ ቃል ትርጕም በትክክል አይታወቅም::

ጥቃት ነጻ መውጣትን ነው፤ በኢሳ52፥7 ከባቢሎናውያን ምርኮ ነጻ መውጣትን፣ ሲያመለክት በሮሜ 10፥15 ደግሞ በክርስቶስ ወንጌል ከኀጢአት ነጻ መውጣትን ያመለክታል:: *በዓላትህን አክብር፤* ነጻ ከመውጣት ደስታ የተነሣ ነው:: *ስእለትህንም ፈጽም፤* በጭንቅህ ጊዜ የተሳልከውን ለማለት ነው፤ የመዝ7፥17 ማብ ይመ:: *ከእንግዲህ ክፉዎች አይወሩህም፤* በምናሴ ዘመን የነበረው የአሦራውያን ወረራ የመጨረሻው ነበር:: *ክፉዎች፤* የዘዳ13፥13 ማብ ይመ:: *ፈጽመው ይጠፋሉ፤* ነነዌ በ612 በወደቀች ጊዜ ተፈጸመ (የቍ14ማብ ይመ)::

2፥1 *አጥቂ፤* በተለይ በሲያክሳሬስ አገዛዝ እንዲሁም በናቦፓላሳር አገዛዝ ሥር ያሉትን የባቢሎናውያን አጋር የሆኑትን ሜዶናውያንንና ስካይትያንን ያመለክታል:: *ምሽግሽን "ጠብቂ"..* *"ኀይልሽን" ሁሉ አሰባስቢ፤* ምናልባት ሥላቅ ያለበት ምፀታዊ አነጋገር ሳይሆን አይቀርም:: *መንገድሽን፤* ጠላት የሚመጣበትን ያመለክታል::

2፥2 *እንደ እስራኤል ክብር...የያዕቆብንም ክብር ይመልሳል፤* ተከፍሎ የነበረው ሕዝብ ሁሉ ተመልሶ አንድ ይሆናል::

2፥3 *የወታደሮቹ፤* አጥቂዎቹ (ቍ1) ወይም የነነዌ ሰዎች ሊሆኑ ይችላሉ:: *ቀይ፤* የጋሻዎቹ ቀለም ወይም በላያቸው ላይ ያለው ደም ወይም ላያቸው ላይ ያለው የፀሐይ ነጸብራቅ ሊሆን ይችላል:: *ይወዛወዛል፤* ለውጊያ ዝግጁ መሆኑን የሚያመለክት ነው::

2፥4 *ሠረገሎች... ይከንፋሉ፤* ይህም (1) የአሦርን የጦር ሠረገሎችና አሦራውያን ራሳቸውን ለመከላከል ሲሉ ታይቶ በማይታወቅ ሁኔታ የደመ ነፍስ ጥድፊያ ማድረጋቸውን ያመለክታል፤ ወይም (2) ነነዌን የወረሩ ሠረገሎችን ሊያሳዩ ይችላል:: የነነዌ ወራሪዎችን ሠረገሎች ነው::

2፥5 *ይጠራል (እርሱ)፤* ምናልባት የአሦር ንጉሥ ሊሆን ይችላል:: *ወደ ከተማይቱ ቅጥር፤* 12.8 ኪሎሜትር ርዝመትና 15 መግቢያ በሮች ወዳሉት ወደ ነነዌ ቅጥር ከመድረሱ በፊት 45 ሜትር ስፋት ያለው በውሃ የተሞላ ጥልቅ ጕድጓድ አለ:: ቅጥር ማፍረሻ ግንዲላዎችም ወደ ላይ ተነሥተው ነበር:: *መከላከያ ጋሻውም፤* ተጠቂዎች የሚይዙት ሲሆን በቅጥሩ ላይ ያሉት ወታደሮች ከወራሪዎች የሚወረወርባቸውን ቀስትና ድንጋይ የሚመክቱበት በቈዳ የተለበጠ ጋሻ ነው::

2፥6 *የወንዙ በር፤* ምናልባት በከተማው አድርጎ ወደ ጤግሮስ ወንዝ በሚፈሰው በኮሸር ወንዝ ላይ የተሠሩ ግድቦች ናቸው:: እነርሱም ቀድሞ በቦታው ላይ ያሉ ወይም የወንዙን ውሃ ለማጉልበት በፍጥነት የተሠሩ ሲሆን፤ ቅጥሩን እንዲያፈራርሱ ድንገት ይለቀቃሉ:: *ወደቀ፤* የባቢሎናውያንን ዜና መዋዕል የጻፈ አንድ የጥንት ታሪክ ጸሓፊ የቅጥሩን ክፊል፣ ጐርፍ ይዞት እንደ ሄደና ወራሪው ኀይል በቀላሉ ወደ ከተማይቱ እንደገባ ተናግሮአል::

2፥7 *ሴቶች ባሪያዎቿ፤* ምናልባት የንግድ ቦታቸውና ጣዖታቸው የፈራረሱባቸው የቤተ ጣዖት ዝሙት አዳሪዎች ሳይሆኑ አይቀርም::

2፥8 *እንደ ኵሬ...ውሃዋም ይደርቃል፤* አንዳንዶች ይህ ጠግሮስንና በከተማዪቱ ዙሪያ የተወሰነ ክፍል የሚፈሱትን ትናንሽ ወንዞች እንዲሁም ከተማዪቷ ፈጽሞ የማትበገር እንድትሆን የሚያደርጓትን የግድቦቹን አሠራር ያመለክታል ብለው ያስባሉ:: ሌሎች ደግሞ አባባሉን በቀሙ ሳይተረጕሙ ውሃ ከኵሬ እንጥፍጥፍ ብሎ እንደሚፈስ ጥርግርግ ብለው የሚሸሹትን የነነዌን ሰዎች ያመለክታል ይላሉ::

*2፥9፤* የወራሪዎችን ጩኸት ያመለክታል::

2፥10 *ተበዝብዛለች፤ ተዘርፋለች፤ ተራቍታለች፤* በዕብራይስጥ እነዚህ ሦስቱ ቃሎች በአንድ ቃል ይወከላሉ:: የባቢሎናውያን ዜና መዋዕል፣ ወራሪዎች አያሌ ንብረት ዘርፈው እንደወሰዱ ያመለክታል:: *ልብ ቀልጦአል፤* ጨካኞቹና ባለጌዎቹ የነነዌ ሰዎች በፍርሀት የሚይዙትንና የሚጨብጡትን አጡ::

*2፥11-13፤* ናሆም ዘይቤአዊ በሆነ አገላለጽ የነነዌን ከተማ የቀድሞ ክብርና ኀይል፣ ምፀታዊ በሆነ አነጋገር ከውድመቷና ከጥፋትዋ ጋር ያነጻጽራል::

2፥11 *ወንዱና ሴቷ አንበሳ፤* ከኢሳ 5፥29፤ ከኢር4፥7፤ ከሆሴ 5፥14፤ ከሚክ 5፥8 ጋር ያነጻጽሩ:: የአሦር ነገሥታት ስግብግብና ዘራፊዎች ከመሆናቸው የተነሣ እንዲሁም የነነዌ ከተማ በአንበሳ ምስል ቅርጻ ቅርጾች በመሞላቷ፣ አሦር በአንበሳ መመሰሏ ትክክለኛ ነው::

[12]አንበሳው ለግልገሎቹ የሚበቃውን ያህል
ገደለ፤
ለእንስቶቹም ዐንቆ ገደለላቸው፤
የገደለውን በማረፊያ ቦታው፣
የነጠቀውንም በዋሻው ሞልቶታል።

[13]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ
ይላል፤
"በእናንተ ላይ ተነሥቼባችኋለሁ፤
ሠረገሎቻችሁን አቃጥዬ አጨሳለሁ፤
ደቦል አንበሶቻችሁን ሰይፍ ይበላል፤
የምትበሉትን በምድር ላይ
አልተውላችሁም፤
የመልእክተኞቻችሁም ድምፅ፣
ከእንግዲህ ወዲያ አይሰማም።"

## ለነነዌ

**3** ለደም ከተማ ወዮላት!
ሐሰት፣
ዝረፋም ሞልቶባታል፤
ብዝበዛዋ ተግዞ አያልቅም።
[2]የጅራፍ ድምፅ፣
የመንኰራኵር ኳኳቴ፣
የፈጣን ፈረስ ኮቴ፣
የሠረገሎች ድምፅ ተሰምቶአል
[3]ፈረሰኛው ይጋልባል፤
ሰይፍ ይንቦገቦጋል፤
ጦር ያብረቀርቃል፤
የሞተው ብዙ ነው፤
ሬሳ በሬሳ ሆኖአል፤
ስፍር ቍጥር የለውም፤
መተላለፊያ አልተገኘም።
[4]ይህ ሁሉ የሆነው ቅጥ ባጣች፣
አሳሳችና መተተኛ በሆነች ዘማዊት
ምክንያት ነው፤
እርሷም በዝሙቷ አሕዛብን፣
በጥንቈላዋም ሕዝቦችን ባሪያ ያደረገች
ናት።
[5]የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ
ይላል፤
"እኔ በጠላትነት ተነሥቼብሻለሁ፤
ቀሚስሽን እስከ ፊትሽ እገልበዋለሁ፤
ዕርቃንሽን ለአሕዛብ፣
ኀፍረትሽንም ለነገሥታት አሳያለሁ።
[6]ቍሻሻ እደፋብሻለሁ፤
እንቅሻለሁ፤
ማላገጫም አደርግሻለሁ።
[7]የሚያዩሽ ሁሉ ከአንቺ እየሸሹ፣
'ነነዌ ፈራርሳለች፤ ማን ያለቅስላታል?'
ይላሉ፤
የሚያጽናናሽንስ ከወዴት አገኛለሁ?"
[8]አንቺ በዐባይ ወንዝ አጠገብ ካለችው፣
በውሃ ከተከበበችው፣
ከኖእ አሞን* ትበልጫለሽን?
ወንዙ መከላከያዋ፣
ውሃውም ቅጥሯ ነው።
[9]ኢትዮጵያና ግብፅ ወሰን የለሽ ኀይሏ
ናቸው፤
ፉጥና ሊቢያም ረዳቶቿ ነበሩ።
[10]ይሁን እንጂ በምርኮ ተወሰደች፤
ተሰዳም ሄደች።
በየመንገዱ ማእዘን ላይ፣
ሕፃናቷ ተፈጠፈጡ፤
በመሳፍንቷ ላይ ዕጣ ተጣለ፤
ታላላቅ ሰዎቿ ሁሉ በሰንሰለት ታሰሩ።
[11]አንቺ ደግሞ ትሰክሪያለሽ፤
ትደበቂያለሽ፣
ከጠላትም መሸሸጊያ ትፈልጊያለሽ።
[12]ምሽጎችሽ ሁሉ ሊበሉ እንደ ደረሱ
የመጀመሪያ በለስ ፍሬ ናቸው፤
በሚወዛወዙበት ጊዜ፣
ፍሬዎቹ በበላተኛው አፍ ውስጥ
ይወድቃሉ።

2፥12 ኢሳ37፥18፤ ኤር 4፥7፤51፥34
2፥13 2ሳሙ2፥26፤ መዝ46፥9፤ኢሳ 10፥5-13፤ኤር21፥13፤ሚክ5፥6፤ናሆ3፥5
3፥1 መዝ12፥2፤ሕዝ 22፥2፤ሚክ3፥10
3፥3 2ነገ19፥35፤ ኢሳ 34፥3፤ኤር47፥3
3፥4 ኢሳ23፥17፤ 47፥9፤ሕዝ16፥25-29
3፥5 ኢሳ20፥4፤ 47፥3፤ ኤር13፥22፤ ናሆ2፥13
3፥6 ዘፀ29፥14፤ 1ሳሙ2፥30፤ኢዮ9፥31፤ኢሳ14፥16፤ኤር 51፥37
3፥7 ኢዮ3፥14፤ኢሳ 13፥14፤31፥9፤51፥19፤ ኤር15፥5፤ናሆ1፥1
3፥8 ኢሳ19፥6-9፤ ኤር46፥25፤አሞ6፥2
3፥9 ዘፍ10፥6፤ 2ዜና12፥3፤ሕዝ27፥10፤30፥5
3፥10 2ነገ8፥12፤ ኢዮ6፥27፤ኢሳ 13፥16፤20፥4፤ኤር 40፥1፤ሕዝ24፥6፤ሆሴ 13፥16
3፥11 ኢሳ2፥10፤ 49፥26፤ናሆ2፥1
3፥12 ማሕ2፥13፤ ኢሳ28፥4

*8 አንዳንዶች *ቴብስ* ይላሉ።

2፥12 *የገደለውን በማረፊያ..ሞልቶታል፤* ነነዌ ከተማ ከተሸነፉ አገሮች በጦርነት በተገኘ ምርኮ ተሞልታ ነበር።

2፥13 *አቃጥዬ አጨሳለሁ፤* የነነዌ ውድቀት እውን የሚሆነው በተፈጥሮ ኀይል ወይም በሚወጋት ኀያላን መንግሥታት አማካይነት ሳይሆን፣ በእግዚአብሔር ኀይል የሚፈጸም ነው። ነነዌ ፍርድ ፊት ቀርባ በደለኛ ሆና ስለተገኘች፣ ትጠፋ ዘንድ ተፈርዶባታል። *ድምፅ፣ ከእንግዲህ ወዲያ አይሰማም፤* ይህንኑ ትንቢት ታሪክ አረጋግጦታል።

3፥1 *ለደም ከተማ፤* ነነዌ ያሸነፈቻቸውን ጠላቶች ጨፍጭፋ እንደምትገድል የታወቀ ነው። አሦራውያን በርኅራኄ ቢስነታቸው፣ በጨካኝነታቸውና በዐረመኔ ድርጊቶቻቸው የታወቁ ነበሩ፤ የማረኳቸውን ብዙዎችን ሰይፈዋል፤ በጦር ወግተዋል ወይም አቃጥለዋል።

3፥3 *ሬሳ በሬሳ ሆኖአል፤* የአሦር ንጉሥ ሰልምናሶር ግላሳዊ በጠላት ከተማ መግቢያ ላይ፣ በተቈረጠ የሰው ራስ ፒራሚድ በማቆም ይኩራራ ነበር። ሌሎች የአሦር ነገሥታት የጠላቶቻቸውን ሬሳ እንደ ግንዲላ በማጋደም በአሸነፉአቸው ከተሞች የቅጥር በሮች ላይ ይከምሩ ነበር። ናሆም ስለ ጨካኞቹ አሦራውያን ያደረገው ገለጻ ተገቢ ነው።

3፥4 *ዘማዊት፤* ምናልባት ዋነኛ የፍቅር አምላክ ተብላ የምትታወቀውን የነነዌን ጣዖት ወይም በአጠቃላይ ከተማዪቱን የሚመለከት ነው። የሀብት ብዛትና የተንደላቀቀ ሕይወት ብዙዎችን ወደ ነነዌ ስቦ ነበር። *መተተኛ...በጥንቈላዋም፤* ዘዳ18፥10 ይመ።

3፥5 *ቀሚስሽን እስከ ፊትሽ እገልበዋለሁ፤* ዝሙት አዳሪዎችና ጋለሞታዎች የሚቀጡት ዐይነት ቅጣት ነው።

*3፥6፤* ነነዌ እንደምትዋረድ ያመለክታል።

3፥7 *ማን?...ከወዴት...?* መልስ አዘል ጥያቄዎች ናቸው፤ ነነዌ የሚራራላት እንደማታገኝ ያመለክታል።

3፥8 *ከኖእ አሞን (ቴብስ)፤* የአሞን ከተማ ወይም የአሞን አምላክ ከተማ ማለት ነው። ቴብስ፤ የላይኛው ግብፅ ታላቂቱ ከተማ ናት። ይዞታዋ ዛሬ በሉክሰርና በከርናክ ከተሞች ግዛት ሥር ነው። በ663 ዓ.ቅ.ክ. ይህች ከተማ በአሦራውያን ተደመሰሰች።

3፥9፤ *ፉጥና፤* የግብፅ አጐራባች ስትሆን፣ ስፍራዋ የት እንደ ሆነ አይታወቅም።

3፥10 *ታላላቅ ሰዎችዋ ሁሉ በሰንሰለት ታሰሩ፤* የአሦር ነገሥታት ብዙ ጊዜ ይህን ያደርጉ ነበር፤ ለምሳሌ አሹርባኒፓል የተባለው የአሦር ንጉሥ ስለያዘው አንድ መሪ ሲናገር፣ በውሻ ሰንሰለት አሰርሁት፣ "ከነነዌ በስተ ምሥራቅ በር በውሻ ቤት አኖርሁት" በማለት ያደረገውን ገልጾአል።

3፥11 *ትሰክሪያለሽ፤* ምናልባት ከእግዚአብሔር የቍጣ ጽዋ ጠጥታ ለማለት ነው።

3፥12 *የመጀመሪያ በለስ ፍሬ፤* ድል አድራጊዎች የነነዌን ብልጥግና ለመዝረፍ ያለቸውን ጕጕት ለማሳየት የገባ ዘይቤአዊ አገላለጽ ነው። *ፍሬዎቹ በበላተኛው አፍ*

[13]እነሆ፣ ጭፍሮችሽ፣
ሁሉም ሴቶች ናቸው!
የምድርሽ በሮች፣
ለጠላቶችሽ ወለል ብለው ተከፍተዋል፤
መዝጊያዎቻቸውንም እሳት በልቶአቸዋል።
[14]ለከበባው ውሃ ቅጂ፤
መከላከያሽን አጠናክሪ፤
የሸክላውን ዐፈር ፈልጊ፤
ጭቃውን ርገጪ፤
ጡቡንም ሥሪ።
[15]በዚያ እሳት ይበላሻል፤
ሰይፍ ይቈርጥሻል፤
እንደ ኩብኩባም ይግጥሻል።
እንደ ኩብኩባ እርቢ፤
እንደ አንበጣም ተባዢ።
[16]ከሰማይ ከዋክብት እስኪበልጡ ድረስ፣
የነጋዴዎችሽን ቍጥር አበዛሽ፤
ምድሪቱን ግን እንደ አንበጣ ግጠው
አሟጠጡ፤
ከዚያም በረው ሄዱ።
[17]ጠባቂዎችሽ እንደ አንበጣ፣
መኳንንቶችሽም በብርድ ቀን
በቅጥር ሥር እንደሚቀመጥ ኩብኩባ ናቸው፤
ፀሓይ ሲወጣ ግን ይበራሉ፤
የት እንደሚበሩም አይታወቅም።
[18]የአሦር ንጉሥ ሆይ፤ እረኞችህ[ሀ]
አንቀላፉ፤
መኳንንትህ ዐርፈው ተኙ፤
ሕዝብህ ሰብሳቢ አጥተው፣
በተራራ ላይ ተበትነዋል።
[19]ቍስልህን ሊፈውስ የሚችል የለም፤
ስብራትህም ለሞት የሚያደርስ ነው፤
ስለ አንተ የሰማ ሁሉ፣
በውድቀትህ ደስ ብሎት ያጨበጭባል፤
ወሰን የሌለው ጭካኔህ፣
ያልነካው ማን አለና?

3፥13 ኢሳ19፥16፤ 45፥2፤ናሆ2፥6
3፥14 2ዜና32፥4፤
3፥15 2ሳሙ2፥26፤ ኢሳ27፥1፤ኤር51፥14፤ኢል1፥4
3፥16 ዘፀ10፥13
3፥17 ኤር51፥27
3፥18 1ነገ22፥17፤ መዝ76፥5-6፤ኢሳ 56፥10፤ኤር25፥27
3፥19 ኢዮ27፥23፤ ኢሳ37፥18፤ኤር 30፥13፤ሰቈ2፥15፤ ሚክ1፥9፤ሶፎ2፥15

[ሀ]18 ገዦች ማለት ነው።

ውስጥ ይወድቃሉ፤ የነነዌ ምሽጎች በመጨረሻ በቀላሉ ይደረመሳሉ።

3፥13 *ጭፍሮችሽ ሁሉም ሴቶች ናቸው፤* ደካሞችና ወራሪውን ኀይል ሊቋቋሙት የማይችሉ ናቸው። *መዝጊያዎቻቸውንም፤* የቅጥር በሮቹ መዝጊያዎች ናቸው።

3፥14 *ውሃ ቅጂ፤* ከበባ ከማድረግ በፊት የሚደረግ የተለመደ ዝግጅት ነው። *መከላከያሽን አጠናክሪ፤* ምንም ማድረግ እንደማትችል ለመግለፅ የገባ ምፀት ነው (የ2፥1 ማብ ይመ)።

3፥15 *በዚያ፤* ጠንካራ ምሽጎችሽ ውስጥ ለማለት ነው። *እሳት ይበላሻል፤* በታሪክና በሥነ ቅርስ ጥናት የተረጋገጠ ነው። የአሦር ንጉሥ የሞተው በቤተ መንግሥቱ ላይ በነደደው እሳት ተቃጥሎ ነው።

3፥16 *ከሰማይ ከዋክብት እስኪበልጡ ድረስ የነጋዴዎችሽን ቍጥር፤* የአሦርን የአገር ውስጥንና የውጭን ንግድ ስፋት የሚያመለክት ነው። *ምድሪቱን... አሟጠጡ፤* ነነዌ ችግር ውስጥ በገባችበት ጊዜ ነጋዴዎች የምድሪቱን ሀብት በሙሉ አሟጠጡ፣ የንግድ መስመሮችንም አጠፉ።

3፥17 *አንበጣ፤* ታላቅ መንጋ ሆነው በመምጣት በመንገዳቸው ያገኙትን ሁሉ ስለሚበሉ፣ በጥንት ቅርብ ምሥራቅ የአበሩ ገበሬዎች እጅግ ይፈሯቸው ነበር። ድርጊታቸው በጥፋቷ ዘመን የነነዌ ሹማምንት ከፈጸሙት ብዝበዛ ጋር የሚነጻጸር ዘይቤ ነው። *አይታወቅም፤* ስለዚህ የነነዌ ሹማምንት አድራሻቸው የት እንደ ሆነ እስከማይታወቅ ድረስ ይጠፋሉ። እጅግ በጣም የሚገርመው ለሞ እተ ዓመታት ራሷ የተቀበረችበት ቦታ ሳይታወቅ ቈይቶ፣ እ.ኤ. አ. በ1845 ዓ.ም. የሥነ ቅርስ ተመራማሪዎች በመጨረሻ ስፍራውን ፈልገው ማግኘታቸው ነው።

3፥18 *ንጉሥ ሆይ፤* ነነዌ ልትወድቅ ስትል ንጉሥ የነበረው ሲን ሻር ኢሽኩን ነበር፤ ስለዚህ እነዚህ ቃሎች በትንቢት መልኩ እርሱን የሚያመለክቱ ናቸው። *እረኞችህ፤* መሪዎችን ማለት ነው። *ዐርፈው ተኙ፤* ሞቱ ማለት ነው። *ሕዝብህ...ተበትነዋል፤* ከጥንት ዘመን ጀምሮ ጥፋት በሚደርስበት ጊዜ የተለመደው የስደተኞች ፍልሰት በነነዌም ተከሥቶአል።

3፥19 *ስብራትህ ለሞት ያደርሳል፤* እንደ ገና ልትሠራ እስከማትችል ድረስ ነነዌ ፈጽማ ተደመሰሰች፤ ከጥቂት መቶ ዓመታት በኋላም ነፋስ ባመጣው አሸዋ ተሸፍና ተቀበረች። ስለዚህ ታላቋ ከተማ (የዮና1፥2 ይመ፤ ከ3፥2 ጋር ያነጻጽሩ)፣ በነቢዩ በናሆም በኩል የተነገረው የእግዚአብሔር ቃል ይፈጸም ዘንድ እንደ ገና ሳትነሣ በ612 ዓ.ቅ.ክ ወደመች።

# ትንቢተ ዕንባቆም

## መግቢያ

### ጸሓፊው

በእስራኤል ሃይማኖታዊ ትውፊት ሥር የሰደደ ጠንካራ እምነት የነበረውና በኤርምያስ ዘመን የኖረ ከመሆኑ በስተቀር፣ ስለ ዕንባቆም ብዙ የሚታወቅ ነገር የለም።

### የተጻፈበት ጊዜ

ባቢሎናውያን መጥተው እንደሚወሩ የተነገረው ትንቢት (1፥6)፣ ዕንባቆም በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት መጨረሻ አካባቢ (640-609 ዓ.ቅ.ክ) ወይም በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት መጀመሪያ ላይ (609-598 ዓ.ቅ.ክ) በይሁዳ ይኖር እንደ ነበር ያመለክታል። ትንቢቱ የተነገረው ከካርከሚሽ ጦርነት (605 ዓ.ቅ.ክ) ጥቂት ቀደም ብሎ ወይም በኋላ ነው፤ በዚህ ጦርነት ላይ በናቡከደነፆርና በናቦፖላሳር የሚመራው የባቢሎን ሰራዊት ቀደም ሲል ከመጨረሻው የአሦር ንጉሥ ጐን በመቆም የተዋጋውን የግብፅን ሰራዊት ሙሉ በሙሉ ድል አድርጎ እስከ ግብፅ ድንበር ድረስ እያባረረ መቶታል (ኤር 46)። ዕንባቆም እንደ ኤርምያስ፣ ባቢሎናውያን ኢየሩሳሌምን እስከ ወረሩበት ጊዜ ድረስ (597 ዓ.ቅ.ክ) ኖሮ የተናገረው ትንቢት ሲፈጸም ለማየት ዕድል አግኝቶ ሊሆን ይችላል።

### መልእክቱ

ከትንቢት መልእክቶች መካከል ዕንባቆምን የተለየ የሚያደርገው እስራኤልን የሚመለከት የትንቢት ቃል ያካተተ ባለመሆኑ ነው። ይልቁንም በነቢዩና በእግዚአብሔር መካከል የተደረገውን ተዋሥኦ የሚያሳይ ነው። ትንቢተ ዮናስ ደግሞ በእግዚአብሔርና በዮናስ መካከል የተካሄደውን ክርክር ይተርካል። በመጀመሪያዎቹ ሁለት ምዕራፎች ውስጥ ዕንባቆም የእግዚአብሔር አሠራር ትክክል እንደ ሆነ ቢያውቅም፣ ለእርሱ እንቆቅልሽ ስለ ሆነበት ከእግዚአብሔር ጋር ይከራከራል። ለጥያቄው ምላሽ ካገኘ በኋላ ግን እምነት የተሞላበትን አስደሳች ቃል በመናገር መልስ ይሰጣል (ም 3)።

ከእግዚአብሔር ጋር ስለ መታገል የሚናገረው ይህ ታሪክ፣ ስለ እስራኤል የተጻፈ እንጂ ከግል ይዞታነት የሕዝብ ወደ መሆን ደረጃ ከደረሰ አንድ ጽሑፍ ተቀንጭቦ የተወሰደ አይደለም፤ ይህም የእግዚአብሔርን መንገድ ለመረዳት የሚታገሉ፣ በይሁዳ የነበሩት ቅዱሳን የሚያሰሙትን ድምፅ የሚያመለክት ለመሆኑም ጥርጥር የለውም። እግዚአብሔር የሰጠው ምላሽ እንደ ዕንባቆም ግራ ተጋብተው በጥርጣሬ ያሉትን ሁሉ የሚናገር ነበር፣ የዕንባቆም የንስሓ ቃል የሕዝቡ ሁሉ የጸሎት መዝሙር ሆነ (የ3፥1 ማብ ይመ)።

ክፋት፣ ዐመፅና ግፍ በይሁዳ እየተስፋፋ ሳለ፤ እግዚአብሔር ምንም ባለማድረጉ ዕንባቆም ግራ ተጋብቶ ነበር። ጨካኞች ባቢሎናውያንን ተጠቅሞ (1፥6)፣ እግዚአብሔር አንድ ነገር ሊያደርግ እንዳለው በተነገረው ጊዜ የባሰውኑ ግራ ተጋባ፤ "ክፋትን እንዳያይ እጅግ ንጹሕ የሆነ አምላክ (1፥13) ጻድቅ በሆነ ሕዝብ ላይ (1፥13) ፍርዱን ለመፈጸም (1፥12)፣ እንዴት እንዲህ ዐይነት ሕዝብ ይጠቀማል?" በማለት ይጠይቃል።

ነገር ግን እነዚህ ክፉታቸው እጅግ የበዛ አጥፊዎች፣ በመጨረሻ ራሳቸው እንደሚጠፉ እግዚአብሔር ግልጽ ያደርግለታል። ዕንባቆምም በእግዚአብሔር የተስፋ ቃል ላይ በማረፍ በአምልኮ መንፈስ በመሆን እርሱ የሚያደርገውን ይጠብቃል።

### ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ

ጸሓፊው በግልጽና በታላቅ ሐዘን ውስጥ ሆኖ የጻፈ ሲሆን፣ ብዙ የማይረሱ ነገሮችንም አስፍሯል (2፥2፡4፡14፡20፤ 3፥2፡17-19)። መጽሐፉ በብሉይ ኪዳንና በአዲስ ኪዳን መካከል በነበሩት ጊዜያት ታዋቂ ነበር። በሁለቱ የመጀመሪያ ምዕራፎች ላይ የተሠራ ሙሉ የማብራሪያ ጽሑፍ በሙት ባሕር ከተገኙት ጥቅልሎች ጋር ተገኝቶአል ("በሁለቱ ኪዳናት መካከል የነበረው ዘመን" የሚለውን ከገጽ 1422 ላይ ይመ)።

### አስተዋፅኦ

1. አሰያየም (1፥1)
2. ዕንባቆም በመጀመሪያ ያሰማው ሮሮ፤ ይሁዳ ስለ ክፋቷ ሳትቀጣ እስከ መቼ ትቆያለች? (1፥2-4)
3. የእግዚአብሔር መልስ፤ ይሁዳ በባቢሎናውያን ትቀጣለች (1፥5-11)
4. ሁለተኛው የዕንባቆም ሮሮ፤ ቅን ፈራጅ የሆነው እግዚአብሔር ከእነርሱ ይልቅ ጻድቅ የሆነውን ሕዝብ ለመቅጣት ክፉ የሆኑትን ባቢሎናውያንን እንዴት ይጠቀማል? (1፥12-2፥1)
5. የእግዚአብሔር መልስ፤ ባቢሎን ትቀጣለች፤ በእምነት መጽናት ዋጋ አለው (2፥2-20)
6. የዕንባቆም ጸሎት፤ የእግዚአብሔር ቍጣና ምሕረት እንዲገለጽ ከጸለየ በኋላ፣ በእግዚአብሔር እንደሚታመንና እንደሚደሰት ተናግሮ መልእክቱን ይደመድማል (ም 3)።

# 1 ነቢዩ ዕንባቆም የተቀበለው ንግር፤

## የዕንባቆም ማጕረምረም

[2]እግዚአብሔር ሆይ፤ ለርዳታ እየተጣራሁ፣
አንተ የማትሰማው እስከ መቼ ነው?
"ግፍ በዛ" ብዬ እየጮኽሁ፣
አንተ የማታድነው እስከ መቼ ነው?
[3]ስለ ምን በደልን እንዳይ አደረግኸኝ?
እንዴትስ ግፍ ሲፈጸም ትታገሣለህ?
ጥፋትና ግፍ በፊቴ አለ፤
ጠብና ግጭት በዝቶአል::
[4]ስለዚህ ሕግ ላልቶአል፤
ፍትሕ ድል አይነሣም፤
ፍትሕ ይጣመም ዘንድ፣
ክፉዎች ጻድቃንን ይከባሉ::

## የእግዚአብሔር መልስ

[5]"ቢነገራችሁም እንኳ፣
የማታምኑትን እናንተን፣
በዘመናችሁ አንድ ነገር ስለማደርግ፣
እነሆ፤ ሕዝቡን እዩ፤ ተመልከቱም፤
እጅግም ተደነቁ::
[6]የራሳቸው ያልሆኑትን መኖሪያ ስፍራዎች
ለመያዝ፣
ምድርን ሁሉ የሚወሩትን፣
ጨካኝና ፈጣን የሆኑትን፣
ባቢሎናውያንን[ሠ] አስነሣለሁ::
[7]እነርሱም የሚያስፈሩና የሚያስደነግጡ
ናቸው፤
ፍርዳቸውና ክብራቸው፣
ከራሳቸው ይወጣል::
[8]ፈረሶቻቸው ከነብር ይልቅ ፈጣኖች፣
ከማታም ተኵላ ይልቅ ጨካኞች ናቸው::
ፈረሰኞቻቸው በፍጥነት ይጋልባሉ፤
ከሩቅ ስፍራም ይመጣሉ::
ነጥቆ ለመብላት እንደሚቸኵል አሞራ
ይበራሉ፤
[9]ሁሉም ለዐመፅ ታጥቀው ይመጣሉ::
ሰራዊታቸው[ሰ] እንደ ምድረ በዳ ነፋስ
ወደ ፊት ይገሠግሣል፤
ምርኮኞችንም እንደ አሸዋ ይሰበስባል::
[10]ነገሥታትን ይንቃል፤
በገዦችም ላይ ያፌዛል፤
በምሽግ ሁሉ ላይ ይሥቃል፤
የዐፈር ቍልል ሠርቶም ይይዘዋል::
[11]ከዚያም በኋላ እንደ ነፋስ ዐልፎ
ይሄዳል፤
ጕልበታቸውን አምላካቸው ያደረጉ
በደለኞች ናቸው::

## የዕንባቆም ዳግመኛ ማጕረምረም

[12]እግዚአብሔር ሆይ፤ ከዘላለም ጀምሮ ያለህ
አይደለህምን?
የእኔ አምላክ፣ የእኔ ቅዱስ እኛ አንሞትም፤
እግዚአብሔር ሆይ፤ እንዲፈርዱ ሾመሃቸዋል፤
ዐለት ሆይ፤ ይቀጡ ዘንድ ሥልጣን
ሰጠሃቸው::
[13]ዐይኖችህ ክፉውን እንዳያዩ እጅግ ንጹሓን
ናቸው፤
አንተ በደልን መታገሥ አትችልም፤
ታዲያ፣ አታላዮችን ለምን ትታገሣለህ?
ክፉው ከራሱ ይልቅ ጻድቅ የሆነውን
ሲውጠውስ፣
ለምን ዝም ትላለህ?
[14]አንተ ሰዎችን በባሕር ውስጥ እንዳለ ዓሣ፣

1፥1 ናሆ1፥1
1፥2 መዝ6፥3፤13፥12፤22፥12፤ኤር14፥9 ዘካ1፥12
1፥3 ቍ13፤ኢ9፥23፤ መዝ55፥9፤ ኤር20፥8
1፥4 ኢዮ19፥7፤ መዝ119፥126፤ ኢሳ፥23፤5፥20፤ 29፥21፤ሕዝ9፥9
1፥5 ኢሳ29፥9፤ ሐሥ13፥41
1፥6 ዘዳ28፥49፤ 2ነገ24፥2፤ኤር13፥20፤21፥7፤ራእ20፥9
1፥7 ኢሳ18፥7፤ ኤር39፥59
1፥8 ዘፍ49፥27 ኤር4፥13
1፥9 ዕን2፥5
1፥10 2ዜና36፥6፤ ኤር33፥4
1፥11 ኤር4፥11፤12፤ ዳን4፥30
1፥12 ዘፍ21፥33፤ 49፥24፤ዘዐ33፥22፤ መዝ118፥17፤ ኢሳ10፥6፤31፥1፤37፥23
1፥13 ቍ3፤ ኢዮ21፥7፤ መዝ18፥26፤25፥3፤ ሰቆ3፥34፡36

[ሠ]6 ከለዳውያን ማለት ነው::
[ሰ]9 የዕብራይስጡ ቃል ትርጉም በትክክል አይታወቅም::

1፥1 *ነቢዩ፤* ዕንባቆም በ3፥1 ላይ ነቢይ የተባለ ሲሆን፣ ምዕ3ን ከምዕ 1እና2 ጋር የሚያያይዝ ነው:: *ዕንባቆም፤* በዕብራይስጡ የስሙ ትርጉም፣ "የሚያቅፍ" ማለት ነው፤ ነገር ግን በአትክልት ስፍራ የሚገኝ የተክልን ዐይነት የሚያሳይ በባቢሎናውያን ቋንቋ የሚገኝ ስም ሳይሆን አይቀርም:: *ንግር፤* በዚህ ላይ እንደሚገኙት እንደ ሁለቱ ዐይነት ማለት ነው (ቍ5-11፤2፥2-20):: ንግር ብዙውን ጊዜ ይመጣ የነበረው በራእይ ነው:: ንግር በዕብራይስጡ፣ "ሸክም" ማለት ሲሆን፣ በአብዛኛው፣ "መግለጫ" ማለት ሳይሆን አይቀርም፤ ይህ ራእይ በማስጠንቀቂያነት የሚያመለክተው ሊመጣ ስላለው ጥፋት ነው (ከኢሳ15፥1፤ 19፥1፤22፥1 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይሁን እንጂ በዘካ9፥1፤ 12፥1፤ በሚል1፥1 እንደ ተገለጸው ተስፋ ያዘለን መልእክትንም ይጨምራል::

*1፥2-2፥20፤* በነቢዩና በእግዚአብሔር መካከል የተደረገውን ክርክር የሚያመለክት ነው:: መሠረታዊው ሐሳብ ከጥንትም የነበረ ይህም፣"ክፉ ለምን ሳይቀጣ ይቀራል?"፣ "እግዚአብሔር ጸሎትን ሰምቶ ለምን አይመልስም?" የሚል ነው::

1፥2 *ግፍ በዛ፤* በዚህ ጊዜ ይሁዳ ርካታ ቢስ፣ ጨካኝና ብልሹ በነበረው በንጉሥ ኢዮአቄም ሥልጣን ሥር ሳትሆን አትቀርም:: ዕንባቆም በሰባተኛው ምዕተ ዓመት (ዓ.ቅ.ክ) መገባደጃ ላይ የነበረውን ማኅበራዊ ዝቅጠትና መንፈሳዊ ክህደት ይገልጻል::

1፥3 *ትታገሣለህ?* ቍ13 ይመ:: እግዚአብሔር ጭካኔና ግፍን እያየ ዝም ያለ ስለ መሰለው፣ ነቢዩ እጅግ በጣም ግራ ተጋብቶአል::

1፥4 *ሕግ ላልቶአል ... ፍትሕ ድል አይነሣም፤* ምክንያቱም ሀብታም የመሬት ባለቤቶች ፍርድ ቤቶችን በጕቦ ተቈጣጥረው ነበር::

1፥5 *የማታምኑትን፤* የይሁዳ ሰዎች እግዚአብሔር ለአብረተኞች ባቢሎናውያን አሳልፎ ይሰጠናል ብለው አያስቡም ነበር::

*1፥6፤* ነጻነታቸውን እንደ ገና ከአሦር በ626 ዓ.ቅ.ክ ባገኙት የአሦርን ኀይል በ612-605 ዓ.ቅ.ክ ፈጽመው በደመሰሱትና እስከ 539 ዓ.ቅ.ክ ኀያል መንግሥት በሆኑት በኀይለኞቹ ሕዝቦች በባቢሎናውያን፣ ከሓዲው የይሁዳ ሕዝብ መቀጣት ነበረበት፤ በዚህ ዐውደ ምንባብ መሠረት (አማራጭ ትርጕሙን ይመ) ባቢሎናውያን የተባሉት፣ "ከለዳውያን" ናቸው:: *መኖሪያ ስፍራዎች ለመያዝ፤* 2፥6-8 ይመ::

1፥7 *ክብራቸው ከራሳቸው ይወጣል፤* የትዕቢተኝነት ምልክት ነው::

*1፥8፤* ባቢሎን ጠላቶችዋን ያሸነፈችበት ፍጥነት ምሳሌያዊ ንግግር ሆኖአል::

1፥9 *ምርኮኞችንም እንደ አሸዋ ይሰበስባል፤* ባቢሎናውያን ልክ እንደቀደሙት አሦራውያን ባወጡት ብሔራዊ ዐላማ መሠረት፣ አሸንፈው የማረኳቸውን ሰዎች ሁሉ አግዘው ይወስዱ ነበር (2፥5 ይመ)::

1፥10 *የዐፈር ቍልል ሠርቶም፤* የከበባ ዘዴ ነው::

1፥11 *ጕልበታቸውን አምላካቸው ያደረጉ፤* ባቢሎናውያን በወታደራዊ ኀይላቸው የሚተማመኑና የሚመኩ ነበሩ፤ ይህም ወታደራዊ ኀይላቸው አምላካቸው እስከ መሆን ደረሰ (ቍ16 ይመ)::

*1፥12፤* እጅግ ክፉና ኀጢአተኛ በሆነ መንግሥት ይሁዳ የተቀጣችበትን ፍትሕ፣ ዕንባቆም ማስተዋል አልቻለም፤ ባቢሎናውያን ይሁዳን ያሸንፉ ዘንድ ፈጽሞ መፈቀድ እንደሌለበትም ያስባል:: ከዘላለም፤ መዝ90፥2 ይመ:: *እግዚአብሔር ሆይ...ሾምሃቸዋል፤* ነቢዩ ባቢሎን የእግዚአብሔር ፍርድ መፈጸሚያ መሣሪያ መሆኑን አሁን ተገነዘበ (ከኢሳ7፥18-20፤ 44፥28፤ 45፥1 ጋር ያነጻጽሩ)::

*1፥13፤* በእስራኤል የእምነት ዐውድ ውስጥ የተነገረ ሲሆን፣ የክፉን መከሠት በተመለከተ ከጥንት ጀምሮ ያለ ሐሳብ ነው፤ ይኸውም፣ "ጻድቅና ቅዱስ በሆነው አምላክ ሳይገደብ ክፉው ጕልበት እያገኘ እንዲሄድ ለምን ይደረጋል"? የሚል ነው:: *አታላዮች...ክፉው፤* እንዲህ የተባሉት ባቢሎናውያን ናቸው:: *ከራሱ ይልቅ የሆነውን፤* የይሁዳን ሕዝብ ነው::

ገዥ እንደሌላቸውም የባሕር ፍጥረታት
  አደረግህ::
[15]ክፉ ጠላት ሁሉንም በመንጠቆ ያወጣቸዋል፤
  በመረቡ ይይዛቸዋል፤
በአሽክላው ውስጥ ይሰበስባቸዋል፤
  በዚህም ይደሰታል፤ ሐሤትም ያደርጋል::
[16]በእነርሱ ተዝናንቶ ይኖራልና፤
  ምግቡም ሰብቶአል::
ስለዚህ ለመረቡ ይሠዋል፤
  ለአሽክላውም ያጥናል::
[17]*ታዲያ* መረቡን ባለማቋረጥ መጣል፣
  ሕዝቦችንስ ያለ ርኅራኄ መግደል አለበትን?

2 በመጠበቂያ ላይ እቆማለሁ፤
  በምሽጉ ቅጥር ላይ ወጥቼ
    እቈያለሁ፤
ምን እንደሚለኝ፣
  ለክርክሩም[a] የምሰጠውን መልስ ለማወቅ
    እጠባበቃለሁ::

***የእግዚአብሔር መልስ***

[2]*እግዚአብሔርም* እንዲህ ሲል መለሰ፤

"በቀላሉ እንዲነበብ፣
  ራእዩን ጻፈው፤
  በሰሌዳም ላይ ቅረጸው::
[3]ራእዩ የተወሰነለትን ጊዜ ይጠብቃልና፤
  ስለ መጨረሻውም ይናገራል፤
እርሱም አይዋሽም፤
  የሚዘገይ ቢመስልም ጠብቀው፤
  በእርግጥ ይመጣል[b]፤ ከቶም አይዘገይም::

[4]"እነሆ፣ እርሱ ታብዮአል፤
  ምኞቱ ቀና አይደለም፤
  ጻድቅ ግን በእምነት[c] ይኖራል::
[5]በእርግጥ የወይን ጠጅ አታሎታል፤
  ትዕቢተኛ ነው፤ ከቶ አያርፍም፤
እንደ ሲኦል[d] ስስታም ነው፣
  እንደ ሞት ከቶ አይጠግብም፤
ሕዝቦችን ለራሱ ይሰበስባል፤
  ሰዎችንም ሁሉ ማርኮ ይወስዳል::

[6]"*ታዲያ* በእንደዚህ ዐይነቱ ሰው ላይ በማፌዝና በመዘበት እንዲህ እያሉ ሁሉም አይሣለቁበትምን?

"የተሰረቀውንሸቀጥ ለራሱ ለሚያከማች፣
  ራሱን በዐመፅ ባለጠጋ ለሚያደርግ
    ወዮለት!
  ይህ የሚቀጥለውስ እስከ መቼ ነው?"
[7]ባለ ዕዳ[e] ያደረግሃቸው ድንገት
    አይነሡብህምን?
ነቅተውስ አያስደነግጡህምን?
  በእጃቸውም ትወድቃለህ::
[8]አንተ ብዙ ሕዝብ ስለ ዘረፍህ፣
  የተረፉት ሕዝቦች ይዘርፉሃል፤
የሰው ደም አፍሰሃልና፤
  አገሮችንና ከተሞችን፣ በውስጣቸው
    የሚኖሩትን ሁሉ አጥፍተሃል::

[9]"በተጭበረበረ ትርፍ መኖሪያውን ለሚገነባ፣
  ከጠላት እጅ ለማምለጥ፣
  ቤቱን በከፍታ ላይ ለሚሠራ ወዮለት!
[10]የብዙ ሰዎች ነፍስ እንዲጠፉ አሢረሃል፤
  በገዛ ቤትህ ላይ ውርደትን፣ በራስህም
    ላይ ጥፋትን አምጥተሃል::
[11]ድንጋይ ከቅጥሩ ውስጥ ይጮኻል፤
  ከዕንጨት የተሠሩ ተሸካሚዎችም
    ይመልሱለታል::

[a]1 ወይም *በተገሠጽሁ ጊዜ የምሰጠውን ምላሽ*
[b]3 የሚመጣ ሰው እንዳለ የሚያመለክቱ አሉ::
[c]4 *በታማኝነቱ* የሚሉ አሉ:: [d]5 *መቃብር* የሚሉ አሉ::
[e]7 ወይም *አበዳሪ* ነው::

1፥15 ኢዮ18፥8፤ ኢሳ19፥8፤ኤር5፥26፤ 16፥16
1፥16 ኤር44፥8
1፥17 ኢሳ14፥6፤ 19፥8
2፥1 መዝ5፥3፤48፥13 ፤85፥8፤ኢሳ21፥8፤ ሕዝ3፥17
2፥2 ኢሳ30፥8፤ ኤር36፥2፤ሕዝ24፥2፤ ሮሜ4፥24፤ራእ19
2፥3 መዝ27፥14፤ ሕዝ12፥25፤ ዳን8፥17፤11፥27
2፥4 ሕዝ18፥9፤ ሮሜ1፥17፤ገላ3፥11፤ ዕብ10፥3738
2፥5 ምሳ20፥1፤ 27፥20፤30፥1516፤ ኢሳ2፥11፤ዕን1፥9
2፥6 ኢሳ14፥4፤ አሞ2፥8
2፥7 ምሳ29፥1
2፥8 ቍ17፤ ኢሳ33፥1፤ ኤር50፥1718፤ ሕዝ39፥10፤ አብ1፥15፤ዘካ2፥89
2፥9 ኢዩ39፥27፤ኢሳ 10፥14፤ኤር22፥13፤5 1፥13
2፥10 ቍ16፤ ኤር26፥19፤ናሆ3፥6
2፥11 ኢሱ24፥27፤ ዘካ5፥4፤ሉቃ19፥40

1፥15 *በመንጠቆ* የአሞ4፥2 ማብ ይመ:: በመረቡ ይይዛቸዋል፤ በወጥመድ የተያዘ ዓሣ ኀይል እንደሌለው ሁሉ፣ በባቢሎናውያን የሚያዙ ሁሉ እንዲሁ ናቸው:: በመስጴጦምያ የተገኙ ቅሪተ አካሎች፣ ምሳሌያዊ በሆነ አገላለጽ አሸናፊ መሪዎች ጠላቶቻቸውን በዓሣ ወጥመድ እንደያዙ የሚያሳዩ ምስሎችን ያመለክታሉ::

*1፥16፤* የቍ11 ማብ ይመ::

2፥1 *በመጠበቂያዬ ላይ እቆማለሁ፤* አንድ ዘብ በምሽጉ ማማ ላይ ሆኖ የመጣበትን ለመመለስ የሚጠባበቅበትን ሁኔታ የሚያመለክት ነው፤ በዚህ ላይ የተነሣውን ማንኛውም ክርክር (አማራጭ ትርጒሙን ይመ) በእግዚአብሔር ፍትሕ ላይ የቀረበ ጥያቄ ነው:: *በምሽጉ ቅጥር፤* የኢየሩሳሌምን ቅጥሮች ነው::

2፥2-3 *ራእዩን፤* 1ዜና17፥15፤ ምሳ29፥18 ይመ:: የዕብራይስጡ ቃል በተለይ የሚያመለክተው የነቢዩን ራእይ ነው(ለምሳሌ ኢሳ1፥1 ይመ)::

2፥3 *ጠብቀው፤* ቀጥሎ ያለው መልእክት 539 ዓ.ቅ.ክ ስለ ባቢሎን መውደቅ የተነገረ ሲሆን፤ ይህም ዕንባቆም ትንቢቱን በተናገረ ከ66 ዓመት በኋላ ማለት ነው:: እግዚአብሔር ለዕንባቆምና ለይሁዳ የትንቢቱ ፍጻሜ፣ "ቢዘገይም" እርሱና ሕዝቡ መጠበቅ እንዳለባቸው ይነግራቸዋል (3፥16 ይመ)::

2፥4 *እርሱ፤* ባቢሎናውያንን ባጠቃላይ የሚገልጽ ሲሆን፣ በተለይ ንጉሣቸውን የሚያመለክት ነው:: *ጻድቅ ግን በእምነት ይኖራል፤* ምኞታቸው ቅን ካልሆነ ባቢሎናውያን ጋር በማነጻጸር ነው (አማራጭ ትርጒሙን ይመ):: በተጨማሪም ኢሳ26 በተለይም ቍ1-6 ይመ:: ሕዝቡ እግዚአብሔር በሰጠው የመገለጥ ብርሃን መሠረት መቼና እንዴት እንደሚሠራ ልዑል አምላካቸውን በመታመን በትዕግሥት መጠበቅና በእምነት መኖር ይጠበቅባቸዋል:: ይህ ሐረግ ሰዎች በጸጋ ድነዋል (ሮሜ1፥17፤ ገላ3፥11፤ ከኤፌ2፥8 ጋር ያነጻጽሩ) እንዲሁም በእምነትም መኖር አለባቸው (ዕብ 10፥38-39) የሚለውን ትምህርት በአጽንዖት ለመግለጽ ብዙ ጊዜ በአዲስ ኪዳን ተደጋግሞ ተጠቅሶአል:: ይህም በ16ኛው ምእተ ዓመት ለነበረው የፕሮቴስታንት እንቅስቃሴ የተሐድሶ ድምፅ ነበር:: ለብሔራዊ ትድግና ተግባራዊ ሆኖ የነበረው ይኸው መርሕ፣ ለመንፈሳዊ ትድግናም (ድነት) ሊውል ይችላል::

2፥5 *እንደ ሲኦል ስስታም፤* ሲኦል ወይም መቃብር፣ "በቃኝ" ማለትን አያውቅም (ምሳ30፥15-16)::

*2፥6-20፤* ይህ የትንኩሳ ዕብራይስጥ ግጥም፣ እያንዳንዱ ዐሥር ስንኝ (ቍ6-14 እና ቍ15-20) እያንዳንዱ ክፍል ጠንከር ባለ ሥነ መለኮታዊ ዐረፍተ ነገር ይደመድማል (ቍ4-20):: እነዚህ ሁለት ዐረፍተ ነገሮች በአንድ ሆነው በባቢሎን (ቍ6፡9፡12፡19 ይመ፤ ከኢሳ5፥8-23፤ ማቴ23፥13-32፤ ሉቃ6፥24-26፤ ራእ9፥12፡11፥14) ጋር ያነጻጽሩ ላይ በስፋት የተነገሩ አምስት፣ "ወዮታን" የያዙ ናቸው::

2፥6 *ሁሉም አይሣለቁበትምን፤* በባቢሎናውያን ተይዘው ግፍ የደረሰባቸው ወገኖች በተለይም ይሁዳ በጨካኟ ባቢሎን ላይ ያፌዛሉ:: *ወዮለት፤* የባቢሎናውያን ድል የማድረግ ስግብግብነት እዚህ ላይ ተወግዞአል::

2፥8 *የሰው ደም አፍሰሃልና፤* ቍ17 ይመ:: ስለዚህ የባቢሎን ደም ይፈሳል (የዘፍ9፥6 ማብ ይመ )::

2፥9 *ወዮለት፤* ባቢሎናውያን በሕንጻ ሥራቸው የነበራቸው ትምክህት ተወግዞአል:: *ቤቱን በከፍታ ላይ፤* ንስር ማንም ሊደርስበት በማይችል ስፍራ ጐጆዋን እንደምትሠራ፣ ባቢሎናውያንም መንግሥታቸው በማንም ሊሸነፍ እንደማይችል ያስቡ ነበር (አብ3-4 ይመ፤ ከኢሳ14፥4፡13-15 ጋር ያነጻጽሩ)

2፥11 *ድንጋይ ... ይጮኻል፤ ... ተሸካሚዎችም፤* ባቢሎናውያን ቤቶቻቸውን የሚሠሩባቸው ድንጋዮችና ተሸካሚዎች በዝርፊያ የተገኙ ነበሩ፤ ስለዚህ በዘረፏቸው ሰዎች ላይ ይመሰክራሉ ማለት ነው::

[12]“ከተማን ደም በማፍሰስ ለሚሠራ፣
በወንጀልም ለሚመሠርታት ወዮለት::
[13]ሰዎች ለእሳት ማገዶ እንዲሆን እንዲለፉ፣
ሕዝቦችም በከንቱ እንዲደክሙ፣
እግዚአብሔር ጸባኦት ወስኖ የለምን?
[14]ውሃ ባሕርን እንደሚሸፍን ሁሉ፣
ምድርም የእግዚአብሔርን ክብር በማወቅ
ትሞላለችና::

[15]“ጎፍረተ ሥጋቸውን ለማየት፣
ባልንጀሮቹን ለሚያጠጣ፣
እስኪሰክሩም ድረስ ወይን ለሚቀዳላቸው
ወዮለት!
[16]በክብር ፈንታ ዕፍረት ትሞላለህ፤
አሁን ደግሞ ተራው የአንተ ነውና፤ ጠጣ፤
ጎፍረተ ሥጋህም ይገለጥ፤
በእግዚአብሔር ቀኝ እጅ ያለው ጽዋ
ይመለስብሃል፤
ክብርህንም ውርደት ይሸፍነዋል::
[17]በሊባኖስ ላይ የሠራኸው ግፍ ያጥለቀልቅሃል፤
እንስሳቱን ማጥፋትህም ያስደነግጥሃል፤
የሰው ደም አፍሰሃልና፤
አገሮችንና ከተሞችን በውስጣቸው
የሚኖሩትንም ሁሉ አጥፍተሃልና::
[18]“የሰው እጅ የቀረጸው ጣዖት፣
ሐሰትንም የሚናገር ምስል ምን ፋይዳ
አለው?
ሠሪው በገዛ እጁ ሥራ ይታመናልና፣
መናገር የማይችሉ ጣዖታትን
ይሠራልና::
[19]ዕንጨቱን፣ ‘ንቃ!’
ሕይወት የሌለውንም ድንጋይ፣ ‘ተነሣ!’
ለሚል ወዮለት፤
በውኑ ማስተማር ይችላልን?
እነሆ፤ በወርቅና በብር ተለብጦአል፤
እስትንፋስም የለውም::
[20]እግዚአብሔር ግን በተቀደሰ መቅደሱ አለ፣
ምድር ሁሉ በፊቱ ጸጥ ትበል::”

## የዕንባቆም ጸሎት

**3** በዝማሬ የቀረበ የነቢዩ የዕንባቆም ጸሎት፤ በሸግዮኖት[ሀ]

[2]እግዚአብሔር ሆይ፤ ዝናህን ሰምቻለሁ፤
እግዚአብሔር ሆይ፤ ሥራህም አስፈራኝ፤
በእኛ ዘመን አድሳቸው፤
በእኛም ጊዜ እንዲታወቅ አድርግ፤
በመዓት ጊዜ ምሕረትን አስብ::

[3]እግዚአብሔር ከቴማን፣
ቅዱሱም ከፋራን ተራራ መጣ:: ሴላ[+]
ክብሩ ሰማያትን ሸፈነ፤
ውዳሴውም ምድርን ሞላ::
[4]ጸዳሉ እንደ ፀሓይ ብርሃን ነው፤
ጨረር ከእጁ ወጣ፤
ኀይሉም በዚያ ተሰውሮአል::
[5]መቅሠፍት በፊቱ ሄደ፤
ቸነፈርም እግር በእግር ተከተለው::

ሀ የሥነ ጽሑፍ ወይም የሙዚቃ ቋንቋ ሳይሆን አይቀርም
+3 ትርጉሙ በትክክል የማይታወቅ ቢሆንም የዜማ ቃል ሳይሆን አይቀርም

2፥12 ሕዝ22፥2፤ ሚክ3፥10
2፥13 ኢሳ47፥13፤ 50፥11
2፥14 ዘፀ16፥7፤ ዘኍ14፥21፤ኢሳ11፥9
2፥15 ምሳ23፥20
2፥16 ቍ10፤ዘሌ 10፥9፤መዝ16፥5፤ኢሳ 51፥22፤ሰቆ4፥21፤ሕዝ 23፥32:34፤ሆሴ4፥7
2፥17 ቍ8፤ ኤር50፥15፤51፥35
2፥18 ዘሌ26፥1፤ መሳ10፥14፤1ሳሙ 12፥21፤መዝ115፥45፤ ኢሳ40፥19፤ኤር5፥21 ፤10፥14፤14፥22፤ 1ቆሮ12፥2
2፥19 1ነገ18፥27፤ ኤር10፥4፤ዳን5፥4:23 ፤ሆሴ4፥12
2፥20 መዝ11፥4፤ ኢሳ41፥1
3፥1 መዝ7 ርእስ
3፥2 ኢዮ26፥14፤ መዝ44፥1፤85፥6፤90፥ 16፤119፥120፤ ኢሳ54፥8፤
3፥3 ዘፍ36፥11:15፤ ዘኍ10፥12፤መዝ8፥1፤ 48፥10፤ኢሳ31፥1
3፥4 ኢዮ9፥6፤ ኢሳ18፥4
3፥5 ዘሌ26፥25
3፥6 ዘፍ21፥33፤ 49፥26፤ዘዐ19፥18፤ መዝ18፥7፤46፥2፤ 114፥16

2፥12 *ወዮለት፤* የባቢሎናውያን ኢፍትሐዊነት በዚህ ስፍራ ተወግዞአል::

2፥13 *ለእሳት ማገዶ፤* በባቢሎናውያን ጒልበት የታነጹ ከተሞች (ቍ12) በእሳት ይቃጠላሉ::

*2፥14፤* ትዕቢተኛዋን ባቢሎንና ምድራዊ ክብሯን ሁሉ እግዚአብሔር ወደ ፊት ሲደመስስ፣ ታላቁ ክብሩ በዓለም ሁሉ እንዲታወቅ ምክንያት ይሆናል (ዘፀ 14፥4፤ 17-18፤ ኢሳ11፥9፤ ራእ 17፥1-19፥4 ይመ)::

*2፥15፤* ከዘፍ9፥20-22 ጋር ያነጻጽሩ:: *ወዮለት፤* የባቢሎናውያን ጭካኔ ተወግዞአል:: ጎረቤቶቿ ያላቸውን ሀብት ሁሉ አሟጣ የዘረፈችበት ሁኔታ (በኋላም በኢየሩሳሌም ላይ ከፈጸመችው ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ፤ 2ነገ25፥8-21)፣ አንድ ሰው ጎረቤቱን አስክሮ ዕርቃን ሥጋውን በማስቀረት በዕራቍትነት ደስ ለመሰኘት ከሚያደርገው ሁኔታ ጋር ተነጻጽሮአል::

2፥16 *ዕፍረት ትሞላለህ ... ይገለጥ፤* ባቢሎን በሌሎች ላይ ያደረገችውን ግፍ፣ *በእግዚአብሔር* በእርሷ ላይ ብድር ይመልስባታል:: *በእግዚአብሔር ቀኝ እጅ ያለው ጽዋ፤* የመለኮት አጸፋ ቅጣት ምልክት ነው (ኢሳ51፥17:22፤ ኤር25፥15-17፤ ሰቆ4፥21፤ ራእ14፥10፤ 16፥19 ይመ)::

2፥17 *በሊባኖስ ላይ የሠራኸው ግፍ፤* ባቢሎናውያን ቤተ መቅደሶቻቸውንና ቤተ መንግሥታቸውን ለማስጌጥ ሲሉ የሊባኖስን የዝግባ ደን ጨፍጭፈው ሳይወስዱ አልቀረም (ከኢሳ14፥8 ጋር ያነጻጽሩ):: *እንስሳቱን ማጥፋትህም፤* በሊባኖስ ደን ውስጥ የአደን ተግባር ይካሄድ እንደነበር፣ በድንጋይ ላይ የተቀረጹ የአሦራውያን ጽሑፎች ያመለክታሉ፤ ወራሪ ባቢሎናውያንም ይህንኑ ዐይነት ዐደን ሳያካሂዱ አልቀረም:: የባቢሎናውያን አጥፊነት በመሬት ላይና በከተማዎች ብቻ ሳይሆን፣ በማንኛውም ዐይነት የሕይወት ዘርፍ ጭምር ነበር::

2፥18 *ጣዖታትን፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ፣ “ንዑሳን አማልክት” ወይም “ምናምንቴዎች” ተብሎ ተገልጾአል:: (ከኢሳ41፥29፤ 44፥9፤ ከኤር10፥5 ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም ዘፀ20፥4-5፤ በመዝ 115፥4-8 ላይ ጣዖታት የተወገዙበትን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ)::

2፥19 *ወዮለት፤* የባቢሎናውያን ጣዖት አምልኮ ተወግዞአል::

2፥20 *ግን፤* የአሕዛብ፣ የድንጋይና የዕንጨት ጣዖታት (ቍ19) በሕዝቡ ፊት ምንም አይናገሩም፤ ነገር ግን የዓለም ሰዎች ሁሉ በሚፈርደው በእውነተኛው አምላክ ፊት ጸጥ ማለት አለባቸው (ከኢሳ41፥1፤ ከሶፎ1፥7፤ ዘካ2፥13 ጋር ያነጻጽሩ):: *በተቀደሰ መቅደሱ፤* በሰማይ ያለውን ያመለክታል::

*3፥1፤* በትኩረት ሲታይ በዚህ ጸሎት ውስጥ ልመና የሚገኘው በቍ2 ላይ ብቻ ነው፤ ነገር ግን እንደብዙዎቹ የዳዊት መዝሙሮች ትውስታን (ቍ3-5)፣ እርግጠኝነትና መታመንን የሚገልጹ አባባሎች (ቍ16-19) ባሉበት ሰፊ ዐውድ ውስጥ ተናኝተው ይገኛሉ፤ በእርግጥ የዕንባቆም ጸሎት መዝሙር ሆኖ ያገለገለ ይመስላል፤ የመዝሙርን ዐይነት ርእስ (ቍ1)፣ የሙዚቃና የሥነ ጽሑፍ ትእምርቶችን ይመ (ቍ1:3:9:13:19)::

3፥2 *ዝናህን ሰምቻለሁ፤* ዕንባቆም በቍ3-15 የእግዚአብሔርን ታላቅ የማዳን ኀይል የሚዘክረውን የጥንት ግጥም የሚያስታውስ ይመስላል፤ ምናልባትም በቤተ መቅደስ የሰማው ሳይሆን አይቀርም (ቍ16 ይመ)::

3፥3 *እግዚአብሔር ... መጣ* የብሉይ ኪዳን ባለቅኔዎችና ባለቅኔ ነቢያት፣ ከግብፅ የወጡበትን በዓል ሲያከብሩ፣ የእግዚአብሔርን ኀያል ሥራ ባስታወሱ ጊዜ፣ የእግዚአብሔርን አስፈሪ መገለጥ ከተለመደው ምስያ ጋር ያጣምሩታል:: ፍላጻዎቹን በየአቅጣጫው በማስፈንጠር፣ በአስገምጋሚ ደመና ሆኖ ዝናብ በመሬት ላይ እየወረደ፣ ተራሮችም በፊቱ እየተንቀጠቀጡ፣ ከሰማይ ሰራዊቱ ጋር በመውረድ አስፈሪውን ነጐድጓድ ሠረገላው አድርጎ ጋለበ (ዘዳ33፥2፤ መሳ5፥4-5፤ መዝ18፥7-15፤68፥4-10:32-35፤ 77፥16-19፤ ሚክ1፥3-4 ይመ):: እንደ እነዚህ ያሉ ሥዕላዊ አገላለጾች፣ ቀጥሎ ባሉት ጥቅሶች የተመለከቱትን ማጣቀሻዎች አጒልተው ያሳያሉ:: እስራኤላውያን ከግብፅ በወጡበት ጊዜ እግዚአብሔር ከይሁዳ በስተ ደቡብ እንደመጣ ተደርጎ ተገልጦአል:: *ከፋራን ተራራ፤* ዘዳ33፥2 ይመ፤ ምናልባት በኤዶምና በሲና መካከል፣ ከአካባ ባሕረ ሰላጤ በሰሜን ምዕራብና ከቃዴስ በርኔ በስተ ደቡብ ያለ ስፍራ ሳይሆን አይቀርም:: *ምድርን ሞላ፤* የ2፥14 ማብ ይመ::

3፥5 *መቅሠፍት ... ቸነፈር፤* የመለኮት መቅጫ መሣሪያዎች ናቸው (ከዘፀ7፥14-12፥30፤ ዘሌ26፥25፤ መዝ91፥3:6 ጋር ያነጻጽሩ)::

[6]*ቆመ*፤ ምድርን አንቀጠቀጠ፤
ተመለከተ፤ ሕዝቦችን አብረከረከ፤
የዘላለም ተራሮች ተፈረካከሱ፤
የጥንት ኰረብቶችም ፈራረሱ፤
መንገዱ ዘላለማዊ ነው።
[7]የኢትዮጵያ ድንኳኖች ሲጨነቁ፣
የምድያምም መኖሪያዎች ሲታወኩ አየሁ።
[8]*እግዚአብሔር* ሆይ፤ በወንዞች ላይ ተቈጣህን?
መዓትህስ በምንጮች ላይ ነበርን?
በፈረሶችህና በድል አድራጊ ሠረገሎችህ፣
በጋለብህ ጊዜ፣
በባሕር ላይ ተቈጥተህ ነበርን?
[9]ቀስትህን አዘጋጀህ፤
ፍላጻም እንዲመጣልህ አዘዝህ፤
ሴላ
ምድርን በወንዞች ከፈልህ፤
[10]ተራሮች አዩህ፤ ተጨነቁም፤
የውሃ ሞገድ ዐልፎ ሄደ፤
ቀላዩ ደነፋ፤
ማዕበሉንም ወደ ላይ አነሣ።
[11]ከሚወረወሩ ፍላጻችህ፣
ከሚያብረቀርቅ የጦርህ ነጸብራቅ የተነሣም፣
ፀሓይና ጨረቃ በቦታቸው ቆሙ።
[12]በምድር ላይ በመዓት ተመላለስህ፤
ሕዝቦችንም በቍጣ ረገጥሃቸው።
[13]ሕዝብህን ለመታደግ፣
የቀባኸውንም ለማዳን ወጣህ፤
የክፋትን ምድር መሪ ቀጠቀጥህ፤
ከራስ ጠጕሩ እስከ እግሩ ጥፍሩም
ዕርቃኑን አስቀረኸው።
[14]እንደ ዐውሎ ነፋስ ሊበታትኑን የመጣውን፣
ምስኪኑን በስውር በመዋጥ የሚደሰተውን፣
የሰራዊት አለቃ ራስ፣
በገዛ ጦሩ ወጋህ።
[15]ታላላቅ ውሆችን በመናጥ፣
ባሕሩን በፈረሶችህ ረገጥህ።
[16]እኔ ሰማሁ፤ ልቤም ደነገጠብኝ፤
ከንፈሬ ከድምፁ የተነሣ ተንቀጠቀጠ፤
ፍርሀት እስከ ዐጥንቴ ዘልቆ ገባ፤
እግሬም ተብረከረከ፤
ሆኖም በሚወረን ሕዝብ ላይ እስኪመጣ
ድረስ፣
የጥፋትን ቀን በትዕግሥት እጠባበቃለሁ።
[17]ምንም እንኳ የበለስ ዛፍ ባያፈራ፣
ከወይን ተክልም ፍሬ ባይገኝ፣
የወይራም ዛፍ ፍሬ ባይሰጥ፣
ዕርሻዎችም ሰብል ባይሰጡ፣
የበጎች ጕረኖ እንኳ ባዶውን ቢቀር፣
ላሞችም በበረት ውስጥ ባይገኙ፣
[18]እኔ ግን *በእግዚአብሔር* ደስ ይለኛል፤
በድነቴ አምላክ ሐሤት አደርጋለሁ።
[19]ጌታ *እግዚአብሔር* ኀይሌ ነው፤
እግሮቼን እንደ ዋላ እግሮች ያደርጋል፤
በከፍታዎችም ላይ ያስሄደኛል።

ለመዘምራን አለቃ፣ በባለ አውታር መሣሪያዎቼ የተዘመረ መዝሙር።

3፥7 ዘኍ25፥2፤ ዘፀ15፥14፤ዘኍ25፥15፤መሳ7፥2425
3፥8 ዘፀ7፥20፤ 2ነገ2፥11፤መዝ68፥17፤77፥16
3፥9 ዘዳ32፥23፤ መዝ7፥1213
3፥10 መዝ77፥16፤ 93፥3፤98፥7
3፥11 ኢሱ10፥13፤ መዝ18፥14፤144፥6፤ ዘካ9፥14
3፥12 ኢሳ41፥15
3፥13 ዘፀ13፥21፤ 2ሳሙ23፥1፤መዝ20፥6፤28፥8፤68፥21፤ 110፥6
3፥14 መሳ7፥22 መዝ64፥25
3፥15 ዘፀ15፥8፤ ኢዮ9፥8
3፥16 ኢዮ4፥14፤ መዝ37፥7
3፥17 ኤር5፥17፤ ኢል1፥1012፡18
3፥18 ዘፀ15፥2፤ መዝ97፥12፤ ኢሳ61፥10፤ሉቃ1፥47፤ፊል4፥4
3፥19 ዘዳ32፥13፤ 33፤29፤መዝ18፥33፤ 46፥15

*3፥6፤* ህለወተ እግዚአብሔር በተደጋጋሚ የተገለጸው በምድር መንቀጥቀጥ ነው (ዘፀ19፥18፤ መዝ18፥7፤ ኤር4፥24፡26፤ 10፥10 ይመ)። የመሬት መንሸራተትም ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ በዚህ ስፍራ ተገልጿል።

3፥7 *ሲጨነቁ፤ ... ሲታወኩ፤* እስራኤላውያን በሙሴ አማካይነት ከግብፅ ነጻ ሲወጡ፣ በጎረቤት ያሉ ሕዝቦች በፍርሀት ተውጠው ነበር (ዘፀ15፥14-16፤ ኢሱ2፥9-10 ይመ)።

*3፥8፤* ኢርቱዕ በሆነ ቅኔያዊ አገላለጽ በዐባይ ላይ የወረደውን መቅሠፍት (ዘፀ7፥20-24)፣ የዮርዳኖስን ቀጥ ብሎ መቆምና (ኢሱ3፥15-17) የቀይ ባሕርን መከፈል ያሳያል (ዘፀ14፥15-31)። ሆኖም በቍ3 ላይ ያለውን ማብ ይመ።

3፥9 *ቀስትህን፤* ምናልባት ከሰማያዊው ቀስተኛ የሚወረወረውን መብረቅ ሊሆን ይችላል። *ምድርን በወንዞች ከፈልህ፤* አብሮ በተከሠተው መብረቅ የተፈጸመ ነው።

3፥11 *ፀሓይና ጨረቃ... ቆሙ፤* በገባዖን ምድር የተገኘውን ድል ኢርቱዕ በሆነ መንገድ ሳያመለክት አይቀርም (ኢሱ10፥12-13)፤ እግዚአብሔር በጠላቶቹ ላይ የሚኖረው ድል በዚያን ጊዜ ፍጹም እንደ ነበር ሁሉ፣ በዚህም ጊዜ እንዲሁ ይሆናል።

3፥12 *ረገጥሃቸው፤* የአሞ1፥3 ማብ ይመ።

3፥13 *ሕዝብህን ለመታደግ፤* እግዚአብሔር የከነዓንን ሕዝብ ተዋግቶ (ቍ12) ሕዝቡን ነጻ አውጥቶአል። *ለማዳን፤* ድልን በመስጠት ማለት ነው። *የቀባኸውን፤* የቃል ኪዳኑ ሕዝብ ማለትም "መንግሥቱ ካህናት" (ዘፀ19፥6) እግዚአብሔርም የታደገው ሕዝብ ማለት ነው። ጠላትን አጥፍቶአል፤ በዚህ ታላቅ ቍጣም (ቍ12) ምሕረትን አስቦአል (ቍ2)። *የክፋትን ምድር መሪ፤* ፈርዖንን ለማለት ነው (ዘፀ14፥5-9 ይመ)

*3፥14-15፤* ግብፃውያን በቀይ ባሕር ስለ መጥፋታቸው ሌላ ማስረጃ ነው፤ እንዲሁም እግዚአብሔር አሁን ያሉትን ጠላቶች ያጠፋቸዋል።

3፥15 *በፈረሶችህ፤* ቍ8 ና ማብ ይመ።

*3፥16፤* ስለ እስራኤል እግዚአብሔር ጥንት የሠራውን ታላቅ ሥራ የሚያወሱ መዝሙሮችን በመስማት (ቍ3-15)፣ ነቢዩ እጅግ ጥልቅ በሆነ ሁኔታ በመፍራቱ አካሉም እንደ ደከመ ያመለክታል፤ በሌላም በኩል የእግዚአብሔርን የማዳን ተስፋ ቃል ከመስማቱ በፊት፣ ባቢሎን ወደ ይሁዳ መጥቶ ያጠፋታል የሚለውን መልእክት በሰማ ጊዜም የሕመም ስሜት ተሰምቶት ነበር። *በሚወረን ሕዝብ፤* ባቢሎንን ለማለት ነው። *በትዕግሥት እጠባበቃለሁ፤* የ2፥3 ማብ ይመ።

*3፥17፤* አስፈሪ ውጤት ሊያመጣ ይችላል ብሎ በመሥጋት፣ የማይቀረውን የባቢሎናውያንን ወረራና ጥፋት ሳያስብ አልቀረም።

*3፥18-19፤* ዕንባቆም አስፈሪ ሁኔታ የከበደውን ያህል ቢከብድ፣ በእግዚአብሔር ቸርነት ላይ የመታመንን ትምህርት ተምሮአል (2እና4)። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የጽኑ እምነት መግለጫ የሆነውን ትምህርት ማለትም እግዚአብሔር ችግርንና ማጣትን ቢያመጣም እንኳ በአምላኩና በመድኀኒቱ ደስ እንደሚሰኝ ዕንባቆም ገልጿል።

3፥19 *እግሮቼን እንደ ዋላ እግሮች ያጠነክራል፤* እግዚአብሔር ታምኜ በጽናት የምቆምበትን ይሰጠኛል ማለት ነው። *አለቃ፤* በቤተ መቅደስ የሙዚቀኞችና የመዘምራን አለቃ ሳይሆን አይቀርም። ይህ ምዕራፍ ምናልባት በሙዚቃ መሣሪያ ከሚታጀበው የቤተ መቅደስ ጸሎት ጋር ተያይዞ የሚቀርብ ሳይሆን አይቀርም (1ዜና16፥4-7 ይመ)። *በባለ አውታር መሣሪያዎቼ፤* በገናና መሰንቆን ጭምር ማለት ነው (መዝ33፥2፤ 92፥3፤ 144፥9)።

# ትንቢተ ሶፎንያስ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ነቢዩ ሶፎንያስ በይሁዳ ውስጥ ከፍተኛ ስፍራ የነበረው ታዋቂ ሰው ሲሆን፣ ምናልባትም ከንጉሣዊ ቤተ ሰብ ወገን ሳይሆን አይቀርም:: ትንቢቱ የሚጀምረው የጸሐፊውን የትውልድ ሐረግ በመዘርዘር ነው (1፥1)፤ ይህም በዕብራውያን የትንቢት አቀራረብ ያልተለመደ ነው:: ሶፎንያስ፣ ከ715-686 ዓ.ቅ.ክ ታዋቂ የይሁዳ ንጉሥ ከነበረው ከሕዝቅያስ ዘርያ አራተኛው ትውልድ ነው:: ከዚህ በስተቀር ቀደም ስላ ለው ታሪኩ ብዙ የተጠቀሰ ነገር የለም:: ሚክያስ በይሁዳ የነበሩ ተራ ሰዎች ችግር ተሰምቶት በጥንቃቄ የተናገረ ሲሆን፣ ሶፎንያስ የሚናገረው ግን በቤተ መንግሥት አካባቢ ከነበረው ሁኔታ ጋር ቅርበት ስላ ለው የፖለቲካ ጉዳይ የሚያሳይ ነው:: ሶፎንያስ በስምንተኛው ምእተ ዓመት የነበሩ፣ እንደ ኢሳይያስና እንደ አሞጽ ያሉ ነቢያትን አነጋገር ማንጸባረቁ እነርሱ የጻፉትን ጽሑፍ ሳያውቅ እንዳልቀረ ይገመ ታል፤ የወጣቱን የኤርምያስን አገልግሎትም ሳያውቅ አይቀርም::

### የተጻፈበት ጊዜ

በ1፥1 ላይ እንደ ተጠቀሰው፣ ሶፎንያስ ትንቢት የተናገረው በንጉሡ በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት ነበር (640-609 ዓ.ቅ.ክ)፤ ይህም ሶፎንያስ የኖረው ኤርምያስ፣ ናሆምና ምናልባትም ዕንባቆም በነበሩበት ዘመን መሆኑን ያመለክታል:: ትንቢቱ የተነገረው ምናልባት በኢዮስያስ ዘመነ መንግስት መጀመሪያው አካባቢ፣ ንጉሡ ለውጥ ለማድረግ ከመሞከሩና የአሦር ንጉሥ አሹርባኒፓል በ627 ዓ.ቅ.ክ ከመሞቱ በፊት ሳይሆን አይቀርም::

### ታሪካዊ ዳራ

ከትንቢተ ኤርምያስና ከትንቢተ ናሆም መግቢያ "ታሪካዊ ዳራ" የሚለውን ይመ፤ በተጨማሪም 2ነገ 22፥1-23:30፤ 2ዜና 34-35 እና ማብ ይመ::

### የመልእክቱ ዐላማና መሪ ሐሳብ

የጸሐፊው ዐላማ ሊመጣ ያለውን የእግዚአብሔርን ፍርድ ለይሁዳ ማሳወቅ ነበር:: ለዚህም መን ሥኤ የሆነው እስኩቴስ የተባለ ሕዝብ በከነዓን ላይ ድንገተኛ ወረራ ማድረጉ ሊሆን ይችላል:: ይህ ሕዝብ ፈረሰኛና ጨካኝ ሲሆን አመጣጡ በአሁኑ ጊዜ ደቡብ ሩሲያ ውስጥ ከሚገኝ ስፍራ ነበር:: በሰባተኛው ምእተ ዓመት ዓ.ቅ.ክ ከነበሩበት ቦታ በመፍለስ ከካሰስን አቋርጠው በመሄድ በአሦር መንግሥት ሰሜ ናዊ ግዛት ሰፈሩ:: ይህ ሕዝብ አንድ ጊዜ የአሦር ጠላት ሌላ ጊዜ ደግሞ ወዳጅ በመሆን አስቀሎናንና አሽዶድን አጥፍቶ በ620 ዓ.ቅ.ክ ገደማ የሚድትራኒያን ባሕር ዳርቻ ተከትሎ ወደ ደቡብ በኀይል እየገፋ ሄደ፤ ነገር ግን ግብፅ ድንበር ላይ ሲደርሱ ፈርዖን ሳመቲስስ በወሰደው ርምጃ ሊገቱ ችለዋል:: በመጨረሻም ሶፎንያስ የተነበየው ጥፋት በባቢሎናውያን እጅ ተፈጸመ፤ ይህም የሆነው ባቢሎናውያን አሦ ርን አሸንፈው ጥንት የነበራቸውን ኀይል ለአንዴና ለመጨረሻ ከመቱ በኋላ ነበር::

የሶፎንያስ መጽሐፍ ዋነኛ መሪ ሐሳብ እግዚአብሔር ከዳተኛዋን ይሁዳን ጨምሮ አሕዛብን ሁሉ ክፉኛ የሚቀጣበት የጌታ ቀን መምጣት ነው (የኢሳ 2፥11:17:20፤ ኢል 1፥15፤ 2፥2፤ አሞ 5፥18፤ 8፥9 ማብ ይመ)፤ ሶፎንያስ ስለዚያ እጅግ አስጨናቂ የመከራ ሁኔታ የሚናገረው በሌሎች የነቢያት መጻሕፍት እንደ ተገለጠው ሁሉ በሥዕላዊ የአገላለጽ ስልት ነው:: ይሁን እንጂ እግዚአብሔር ተመልሶ ለሕዝቡ ምሕረት እንደሚያደርግ በግልጽ ይናገራል:: ሌሎች ብዙ ነቢያት እንደሚያደርጉት ሁሉ፣ ሶፎንያስም ስለሚመጣው ጥፋት ከተናገረ በኋላ፣ ይሁዳ ተመልሳ እንደምትታደስ በማመልከት ትንቢቱን በተስፋ ቃል ይደመድማል::

### አስተዋፅኦ

1. መግቢያ (1፥1-3)
   ሀ. ርእስ፤ ነቢዩ ማን እንደ ሆነ መገለጹ (1፥1)
   ለ. መቅድም፤ በፍጥረት ሁሉ ላይ የተነገረ ፍርድ (1፥2-3)
2. የጌታ ቀን በይሁዳና በአሕዛብ ላይ ስለመምጣቱ (1፥4-18)
   ሀ. በይሁዳ በሚኖሩ ጣዖት አምላኪዎች ላይ የሚደርሰው ፍርድ (1፥4-9)
   ለ. በኢየሩሳሌም ሁሉ የሚሰማው ወዮታ (1፥10-13)
   ሐ. የማያመልጡት የእግዚአብሔር የቍጣ ቀን (1፥14-18)
3. በአሕዛብ ላይ የሚመጣው የእግዚአብሔር ፍርድ (2፥1-3፥8)
   ሀ. የንስሓ ጥሪ (2፥1-3)
   ለ. በፍልስጥኤም ላይ የሚመጣው ፍርድ (2፥4-7)
   ሐ. በሞዓብና በአሞን ላይ የሚመጣው ፍርድ (2፥8-11)
   መ. በኢትዮጲያ ላይ የሚመጣው ፍርድ (2፥12)
   ሠ. በአሦር ላይ የሚመጣው ፍርድ (2፥13-15)

ረ. በኢየሩሳሌም ላይ የሚመጣው ፍርድ (3፥1-5)
ሰ. ኢየሩሳሌም ንስሓ አልገባም ማለቷ (3፥6-8)

4. የትሩፋኑ መቤዠት (3፥9-20)
ሀ. አሕዛብ ይነጻሉ፤ ትሩፋኑ ተመልሰው ይቋቋማሉ፤ ኢየሩሳሌም ከኀጢአት ትጠራለች (3፥9-13)
ለ. በከተማው ውስጥ ሐሤት ይሆናል (3፥14-17)
ሐ. የአሕዛብ ተመልሰው መደራጀት (3፥18-20)

1 በይሁዳ ንጉሥ በአሞጽ ልጅ በኢዮስያስ ዘመን ወደ ሕዝቅያስ ልጅ፣ ወደ አማርያ ልጅ፣ ወደ ጎዶልያስ ልጅ፣ ወደ ኩሲ ልጅ ወደ ሶፎንያስ የመጣ *የእግዚአብሔር* ቃል ይህ ነው፤

**ስለሚመጣው ጥፋት የተሰጠ ማስጠንቀቂያ**

2 "ማንኛውንም ነገር፣
ከምድር ገጽ አጠፋለሁ"
ይላል *እግዚአብሔር*።

3 "ሰውንና እንስሳን አጠፋለሁ፤
የሰማይን ወፎች፣
የባሕርንም ዓሦች አጠፋለሁ፤
ሰውን ከምድር ገጽ በማስወግድበት ጊዜ፣
ክፉዎች የፍርስራሽ[ሀ] ክምር ይሆናሉ"
ይላል *እግዚአብሔር*።

**በይሁዳ ላይ የተነገረ ጥፋት**

4 "እጄን በይሁዳ፣
በኢየሩሳሌምም በሚኖሩት ሁሉ ላይ
እዘረጋለሁ፤
የበኣልን ትሩፍ፣
የጣዖታቱንና የአመንዝራ ካህናቱን ስም
ሁሉ ከዚህ ስፍራ አጠፋለሁ፤
5 የሰማይን ሰራዊት ለማምለክ፣
በሰገነት ላይ ወጥተው የሚሰግዱትን፣
*ለእግዚአብሔር* እየሰገዱ፣ በስሙም
እየማሉ፣
በሚልኮምም[ለ] ደግሞ የሚምሉትን፣
6 *እግዚአብሔርን* ከመከተል ወደ ኋላ
የሚመለሱትን፣
*እግዚአብሔርን* የማይፈልጉትን፣
እንዲረዳቸውም የማይጠይቁትን
አጠፋለሁ።

7 በልዑል *እግዚአብሔር* ፊት ዝም በሉ፤
*የእግዚአብሔር* ቀን ቀርቦአልና።
*እግዚአብሔር* መሥዋዕት አዘጋጅቶአል፤
የጠራቸውንም ቀድሶአል።
8 *በእግዚአብሔር* የመሥዋዕት ቀን፣
መሳፍንቱንና የንጉሡን ልጆች፣
እንግዳ ልብስ የሚለብሱትን ሁሉ
እቀጣለሁ።
9 በዚያን ቀን፣
በመድረኩ ላይ የሚዘሉትን ሁሉ፣
የአማልክቶቻቸውን ቤት፣
በዐመፅና በማጭበርበር የሚሞሉትን
እቀጣለሁ።

10 *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"በዚያ ቀን ከ'ዓሣ በር' ጩኸት
በሁለተኛው አደባባይ ዋይታ፣
ከኮረብቶችም ታላቅ ሽብር ይሰማል።
11 እናንት በመክቴሽ[ሐ] ገበያ የምትኖሩ
ዋይ በሉ፤
ነጋዴዎቻችሁ ሁሉ ይደመሰሳሉ፤
በብር የሚነግዱትም ሁሉ ይሞታሉ።
12 በዚያ ዘመን ኢየሩሳሌምን በመብራት
እፈትሻለሁ፤
ተንደላቀው የሚኖሩትን፣
በዝቃጩ ላይ እንደ ቀረ የወይን ጠጅ
የሆኑትን፣
'ክፉም ይሁን መልካም፣

1፥1 2ነገ22፥1፤ ዜና3፥14፤2ዜና 34፥1፤5፥25
1፥2 ዘፍ6፥7
1፥3 ቍ18፤ኤር 4፥25፤50፥3፤ሕዝ 14፥17፤ሆሴ4፥3
1፥4 ኤር6፥12፤ 15፥6፤ሆሴ10፥5፤ሚክ 5፥13፤ሶፎ2፥11
1፥5 ዘሌ18፥21፤ ኤር5፥7፤8፥2
1፥6 ኢሳ1፥4፤9፥13 ፤ኤር2፥13፤ሆሴ7፥7
1፥7 ቍ14፤ዘሌ 3፥9፤ኢሳ13፥6፤ 41፥1፤ኤር46፥10፤ ሕዝ7፥19፤ኢል 3፥14፤አሞ5፥18-20
1፥8 ኢሳ24፥21፤ ኤር39፥6
1፥9 1ሳሙ5፥5፤ አሞ3፥10
1፥10 2ዜና33፥14፤ ኢሳ22፥5፤አሞ5፥16
1፥11 ሆሴ9፥6፤ ያዕ5፥1
1፥12 2ነገ21፥16፤ ኢዮ22፥13፤ኤር 48፥11፤ሕዝ8፥12፤ አሞ6፥1

[ሀ] 3 የዕብራይስጡ ቃል ትርጒም በትክክል አይታወቅም።
[ለ] 5 በዕብራይስጥ *መልካም* ይባላል
[ሐ] 11 አንዳንዶች *በሞርታር* ይላሉ።

1፥1 *የእግዚአብሔር ቃል፤* በነቢያት መጻሕፍት የሚገኝ የጋራ መግቢያ ነው (ለምሳሌ ኤር 1፥4፤ ሆሴ 1፥1፤ ሚክ 1፥1 ይመ)። *ሶፎንያስ፤* የስሙ ትርጒም፣ "እግዚአብሔር ይከልላል" ወይም "እግዚአብሔር ይጠብቃል" ማለት ነው፤ ይኸውም ከንጉሥ ኢዮስያስ በፊት በነገሡት ክፉ መሪዎች ማለትም በምናሴና በአሞን ዘመነ መንግሥት፣ እግዚአብሔር ሶፎንያስን ስለ ጠበቀው ሊሆን ይችላል። *ወደ ሕዝቅያስ ልጅ፤* ምሁራን የነቢዩን የትውልድ ሐረግ በማስተዋል ሶፎንያስ ትንቢቱን መናገር ሲጀምር ዕድሜው ሃያ ዓመት ገደማ እንደ ነበር ይናገራሉ፤ ነቢዩ ኢሳይያስ የመሳፍንት ወገን ሳይሆን አይቀርም ከመባሉም ሌላ፣ በሸንጎ አደባባይ አዘውትሮ ይመላለስ ነበር፤ ሶፎንያስ ግን ከኢሳይያስ ይልቅ ከገዥው ወገን እንደ ነበር ይነገርለታል።

1፥2-3 *አጠፋለሁ፤* እግዚአብሔር ከጥፋት ውሃ በፊት (ዘፍ 6፥7) ሲናገር የተጠቀመበትን አገላለጽ በማስታወስ፣ ሶፎንያስ ሊመጣ ስላለው ጥፋት ይናገራል። በዚህ ጊዜ ግን፣ ጥፋቱ የሚከናወነው ከእግዚአብሔር በተላከች እሳት ይሆናል (ቍ 18፤ 3፥8)።

1፥3 *የፍርስራሽ ክምር፤* አማራጭ ትርጒሙን ይመ። እግዚአብሔር በክፉዎች ፊት መሰናክል ያኖራል፤ ፈጽሞም ያጠፋቸዋል እንደ ማለት ነው።

*1፥4-6፤* እዚህ ላይ የተኰነኑት ልማዶች የተወገዱት በኢዮስያስ የተሐድሶ ዘመን በመሆኑ (2ነገ 23፥4-16)፣ የሶፎንያስ የአገልግሎት ዘመን የነበረው በ621 ዓ.ቅ.ክ. ሳይሆን አይቀርም። ኢዮስያስና ሕዝቡ የተሐድሶውን ተግባር ለማከናወን ይበረታቱ ዘንድ፣ የሶፎንያስ ትንቢት አስተዋጽኦ ሳያደርግ አልቀረም (ከ2ዜና 34፥1-7 ጋር ያነጻጽሩ)።

*1፥4፤* ይሁዳ የተወቀሰችው ራሷን ሙሉ በሙሉ ለበኣል ጣዖት አምልኮ አሳልፋ ሰጥታ እያለ ንስሓ ባለመግባቷ ነው። *ከዚህ ስፍራ፤* ሶፎንያስ የኖረባትን ኢየሩሳሌምን ሳያመለክት አይቀርም። *የበኣልን፤* የሆሴ 2፥13 ማብ ይመ።

1፥5 *በሰገነት ላይ፤* 2ነገ 23፥12፤ ኤር 19፥13 ይመ። *የሰማይን ሰራዊት ለማምለክ፤* ዘፀ 4፥15-19፤ 2ነገ 17፥16፤ 21፥3፤ ኢሳ 47፥13 ይመ። *ለእግዚአብሔር እየማሉ...በሚልኮም፤* የግልን የጣዖት አምላክ ከሌሎች አማልክት ጋር ማምለክ ነው። *በሚልኮም፤* የአሞናውያን አምላክ ሲሆን፣ የልጅ መሥዋዕትም ይቀርብለት ነበር። እስራኤላውያንም ሚልኮምን እንዳያመልኩ ተከልክለዋል (ዘሌ 18፥21፤ 20፥1-5)። ይህ ትእዛዝ ቢሰጥም እንኳ፣ ሰሎሞን በደብረ ዘይት ተራራ ላይ ለሚልኮም መስገጃ ሠርቶአል (1ነገ 11፥7)። ምናሴም በሄኖም ልጅ ሸለቆ የጣዖት አምልኮ ሥርዐቶችን ዘርግቶ ነበር (2ዜና 33፥6፤ ኤር 7፥31፤ 32፥35)።

1፥7 *በልዑል እግዚአብሔር ፊት ዝም በሉ፤* ዕን 2፥20 ይመ። *የእግዚአብሔር ቀን፤* የሶፎንያስ ትንቢት ዐቢይ ሐሳብ ነው (በመግቢያው ላይ "ዐላማና ዐቢይ ሐሳብ" የሚለውን ይመ)። ይህም ይሁዳን ለመታደግ ሳይሆን፣ በጣዖት አምላኪው የኪዳን ሕዝብ ላይ የሚመጣውን የእግዚአብሔርን በቀል ለማመልከት ነው። *መሥዋዕት፤* የምትሠዋ ይሁዳ ናት። *ቀድሶአል፤* በመምጣት ላይ ያለው የዕልቂት ፍርድ መሥዋዕት ነው ከተባለ እግዚአብሔር እንግዶቹን ሲያዘጋጅ ቀድሶአል ይባላል፤ የሚያዘጋጃቸውም በብዝበዛው በዓል ላይ እንዲገኙ ነው። *የጠራቸውንም፤* አረመኔ ወራሪዎች ናቸው (እነርሱም በአብዛኛው ባቢሎናውያን ናቸው)።

1፥9 *በመድረኩ ላይ የሚዘሉትን ሁሉ፤* በሳሙኤል ዘመን የተጀመረውን የአሕዛብ ልማድ የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (አማራጭ ትርጒሙን ይመ)።

*1፥10-13፤* ከተማዋ ዳር እስከዳር በሐዘን ድምፅ ተሞልታለች (ከ3፥14-17 ጋር ያነጻጽሩ)።

*1፥10፤* በማጭበርበር ሀብት ያካበቱ ነጋዴዎች እንደሚጠፉ ያመለክታል። *ከዓሣ በር፤* የነህ 3፥3 ማብ ይመ። *በሁለተኛው አደባባይ፤* የነህ 11፥9 ማብ ይመ።

1፥11 *በመክቴሽ ገበያ፤* አንዳንድ የውጭ አገር ነጋዴዎች የሚኖሩበት (1ነገ 20፥34 እና ማብ ይመ) ከሞሪያም ተራራ በስተ ደቡብ የሚገኘው የታይሮፓን ሸለቆ ነው።

1፥12 *ኢየሩሳሌምን በመብራት እፈትሻለሁ፤* ከጊዜ በኋላ ባቢሎናውያን እስራኤላውያንን ከተደበቁበት ሁሉ ከቤት፣ ከጕ

*እግዚአብሔር* ምንም አያደርግም'
የሚሉትን ቸልተኞች እቀጣለሁ።
[13]ሀብታቸው ይዘረፋል፤
ቤታቸው ይፈራርሳል፤
ቤቶች ይሠራሉ፤
ነገር ግን አይኖሩባቸውም፤
ወይን ይተክላሉ፤
ጠጁን ግን አይጠጡም።

## ታላቁ የእግዚአብሔር ቀን

[14]"ታላቁ *የእግዚአብሔር* ቀን ቅርብ ነው፤
ቅርብ ነው ፈጥኖም ይመጣል፤
*በእግዚአብሔር* ቀን የሚሰማው ልቅሶ
መራራ ነው፤
በዚያ ጦረኛውም ምርር ብሎ
ይጮኻል፤
[15]ያ ቀን የመዓት ቀን፣
የመከራና የጭንቀት ቀን፣
የሁከትና የጥፋት ቀን፣
የጨለማና የጭጋግ ቀን፣
የደመናና የድቅድቅ ጨለማ ቀን
ይሆናል፤
[16]ያ ቀን በተመሸጉ ከተሞችና፣
በረጃጅም ግንቦች ላይ፣
የመለከት ድምፅና የጦርነት ጩኸት
የሚሰማበት ቀን ይሆናል።
[17]እንደ ዕውር እንዲራመዱ፣
በሰዎች ላይ ጭንቀት አመጣባቸዋለሁ፤
*በእግዚአብሔር* ላይ ኀጢአትን
ሠርተዋልና።
ደማቸው እንደ ትቢያ፣
ሥጋቸውም እንደ ጕድፍ ይጣላል።
[18]*በእግዚአብሔር* የቍጣ ቀን፣
ብራቸውም ሆነ ወርቃቸው፣
ሊያድናቸው አይችልም፤
መላዪቱ ምድር፣
በቅናቱ ትበላለች፤
በምድር በሚኖሩ ሁሉ ላይ፣
ድንገተኛ ፍጻሜ ያመጣባቸዋልና።"

**2** እናንት ዕረፍት የሌላችሁ ሕዝብ ሆይ፤
በአንድነት ተሰብሰቡ፤ ተከማቹም፤
[2]የተወሰነው ጊዜ ሳይደርስ፣
ቀኑ እንደ ገለባ ሳይጠራርጋችሁ፣
*የእግዚአብሔር* ጽኑ ቍጣ በእናንተ ላይ
ሳይመጣ፣
*የእግዚአብሔር* የመዓት ቀን
ሳይደርስባችሁ ተሰብሰቡ።
[3]እናንት የምድር ትሑታን ሁሉ፣
ትእዛዙን የምትፈጽሙ፣ *እግዚአብሔርን*
እሹ፤
ጽድቅንና ትሕትናን ፈልጉ፤
*በእግዚአብሔር* የቍጣ ቀን፣
ትሰወሩ ይሆናል።

## በፍልስጥኤም ላይ የተነገረ ጥፋት

[4]ጋዛ ባድማ ትሆናለች፤
አስቀሎናም ፈራርሳ ትቀራለች፤
አዛጦን በቀትር ባዶ ትሆናለች፤
አቃሮንም ትነቀላለች።
[5]እናንት በባሕር ዳርቻ የምትኖሩ፣
የከሊታውያን ሰዎች ሆይ፤ ወዮላችሁ!
የፍልስጥኤማውያን ምድር ከነዓን ሆይ፤
በአንቺ ላይ የተነገረው *የእግዚአብሔር*
ቃል ይህ ነው፤
"ፍጹም አጠፋሻለሁ፤
ከነዋሪዎችሽም የሚተርፍ የለም።"
[6]የቀርጤስ[m] ሰዎች የሚኖሩበት በባሕሩ ዳር
ያለው ምድር፣
የእረኞች መኖሪያና የበጎች በረት
ይሆናል፤
[7]ይህም ለይሁዳ ቤት ትሩፍ ይሰጣል፤
እነርሱም በዚያ መሰማሪያ ያገኛሉ።
በአስቀሎና ቤቶች ውስጥም፣
በምሽት ይተኛሉ፤
ስምባካቸው *እግዚአብሔር* ይጠብቃቸዋል፤
ምርኮአቸውንም ይመልስላቸዋል።

## በሞዓብና በአሞን ላይ የተነገረ ጥፋት

[8]"የሞዓብን ስድብ፣
የአሞናውያንንም ፌዝ ሰምቻለሁ፤
ሕዝቤን ሰድበዋል፤

[m]6 የዕብራይስጡ ትርጕም በትክክል አይታወቅም።

1፥13 ዘዳ28፥30፡39፤2ነገ24፥13፤ኤር 15፥13፤ሰቆ5፥2፤ አሞ5፥11
1፥14 ቍ7፤ሕዝ 7፥7፤ዳን7፥13፤ ኢዩ1፥15
1፥15 1ሳሙ2፥9፤ ኢሳ22፥5፤ኢዩ2፥2፤ ማር13፥2425
1፥16 ዘዳ28፥52፤ ኢሳ2፥15፤ኤር 4፥19፤ኢዩ2፥1
1፥17 ዘዳ28፥52፤ መዝ79፥3፤83፥10፤ ኢሳ59፥10
1፥18 ቍ23፤ዘፍ 6፥7፤ዘዳ29፥20፤ ኢዮ20፥20፤40፥11፤ ኤር4፥4፤ሕዝ7፥11፡ 19፤ሶፎ3፥8
2፥1 2ዜና20፥4፤ ኤር3፥3፤6፥15፤ ኢዩ1፥14
2፥2 ኢሳ17፥13፤ ኤር4፥4፤10፥25፤ ሰቆ4፥11፤ሕዝ 7፥19፤ሆሴ13፥3
2፥3 መዝ45፥4፤ 57፥1፤ኢሳ1፥17፤ አሞ5፥6
2፥4 ዘፍ10፥19፤ ኤር47፥5፤አሞ1፥6፡ 7-8፤ዘካ9፥57
2፥5 ዘሌ26፥31፤ 1ሳሙ30፥14፤ኢሳ 14፥30፤አሞ3፥1
2፥6 ኢሳ5፥17
2፥7 ዘፍ45፥7፤ዘዳ 30፥3፤መዝ126፥4፤ ኤር32፥44፤ሆሴ6፥11 ፤ኢዩ3፥1፤አሞ1፥68
2፥8 ዘፍ19፥37፤ ኢሳ16፥6፤ኤር 48፥27፤ሰቆ3፥61፤ ሕዝ21፥28፤25፥3

ዳና፣ ከሠገራ ቱቦዎችና ከመቃብሮች እየጐተቱ አወጡአቸው። *እግዚአብሔር ምንም አያደርግም፤* የከፉዎችን ማንነት አጕልቶ የሚያሳይ ዕውቅ አገላለጽ ነው (የመዝ 10፥11 ማብ ይመ)።

*1፥13፤* በማጭበርበር የተከማቸው ሀብት ይጋለጣል፤ ይዘረፋልም (ዘዳ 28፥30 ይመ)።

*1፥14-18፤* ጌታ በሚያስደንቅና ልብን በሚማርክ አባባል የዓለም ጥፋት በእግዚአብሔር የፍርድ ቀን ምን እንደሚመስል ይገልጻል።

1፥15 *የጨለማና የጭጋግ፤* አሞ 5፥18-20 ይመ።

1፥17 *እንደ ዕውር፤* ዘዳ 28፥28-29 ይመ።

1፥18 *ብራቸውም ሆነ ወርቃቸው ሊያድናቸው አይችልም፤* በእግዚአብሔር የፍርድ ቀን ምድራዊ ሀብት ከቅጣት ሊታደግ አይችልም።

*2፥1-3፤* ሕዝቡ ንስሓ ይገባ ዘንድ ነቢዩ ጥሪ ያቀርባል፤ ይህ የንስሓ ጥሪና ኢየሩሳሌም ለንስሓ እምቢተኛ በመሆኗ የቀረበባት ክስ (3፥6-8 እና ማብ ይመ)፣ ወደ ፊት በሚመጣው የጌታ ቀን በሚፈጸመውንና ሥዕላዊ በሆነ ሁኔታ የእግዚአብሔርን ሥራ የሚገልጸውን ተከታታይ ፍርድ ዐቅፎ የያዘ ነው (2፥4-3፥5)።

2፥2 *እንደ ገለባ፤* የመዝ 1፥4 ማብ ይመ።

2፥3 *እግዚአብሔርን እሹ፤* ጥፋት መምጣቱ የማይቀር ቢሆንም እንኳ፣ ሕዝቡ ንስሓ ከገባ ሊመጣ ካለው ጥፋት ለመጠበቅ አሁንም ዕድሉ አለ። *ትሑታን፤* በባዕድ አምልኮታቸውና በክፋታቸው መከራራትን ትተው ንስሓ በመግባት ራሳቸውን በእግዚአብሔር ፊት የሚያዋርዱትን ያመለክታል።

*2፥4-3፥8፤* ኢየሩሳሌምን ጨምሮ በሕዝቦች ላይ ሊመጣ ያለውን የእግዚአብሔርን ፍርድ ያመለክታል (ከአሞ 1-2 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥4 *ጋዛ…አስቀሎናም…አዛጦን…አቃሮንም፤* የኢሱ 13፥3፤ የመሳ 3፥3፤ የአሞ 1፥6፡8 ማብ ይመ።

2፥5 *የከሊታውያን፤* የ1ሳሙ 30፥14 ማብ ይመ። *ከነዓን፤* የዘፍ 10፥6 ማብ ይመ። *የሚተርፍ፤* የጌታን ዐላማ ይገልጻል።

*2፥6፤* አያሌ ሕዝብ ይኖርባቸው የነበሩት የፍልስጥኤም ከተሞች ተመልሰው የግጦሽ ቦታዎች ይሆናሉ።

*2፥7፤* ታማኝ የሆኑት የይሁዳ ቅሬታዎች ይህችን ምድር በመያዝ የበግና የፍየል መንጋቸውን ለግጦሽ ያሰማሩበታል። *ምርኮአቸውንም ይመልስላቸዋል፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። እዚህ ላይና በቍ 9:11 ላይ የጌታ ቀን ሲመጣ ውጤቱ ምን እንደሚመስል በአሻጋሪ ያመለክታል፤ ይህንም በ3፥9-20 በደበልጥ አጕልቶአል።

2፥8 *የሞዓብን…የአሞናውያንንም፤* የዘፍ 19፥36-38፤ የአሞ

በምድራቸውም ላይ ዝተዋል።
[9]ስለዚህ የእስራኤል አምላክ፣ ሁሉን የሚገዛ
እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤
"በሕያውነቴ እምላለሁ!
ሞዓብ እንደ ሰዶም፣
አሞናውያን እንደ ገሞራ፣
ዐረም እንደ ዋጠው ቦታና እንደ ጨው
ጒድጓድ
ለዘላለም ጠፍ ይሆናሉ።
ከሕዝቤ የቀሩት ይዘርፏቸዋል፤
ከወገኔ የተረፉትም ምድራቸውን
ይወርሳሉ።"
[10]ከትዕቢታቸው የተነሣ የሚደርስባቸው
ይህ ነው፤
የሁሉን ገዥ የእግዚአብሔርን ሕዝብ
ሰድበው ዘብተውበታልና፣
[11]እግዚአብሔር የምድሪቱን አማልክት ሁሉ
በሚደመስስበት ጊዜ፣
በእነርሱ ዘንድ የተፈራ ይሆናል፤
በየባሕሩ ጠረፍ የሚኖሩ ሕዝቦች፣
እያንዳንዳቸው በያሉበት ሆነው ለእርሱ
ይሰግዳሉ።

## በኢትዮጵያ ላይ የተነገረ ጥፋት

[12]"ኢትዮጵያውያን ሆይ፤ እናንተም፣
በሰይፌ ትገደላላችሁ።"

## በአሦር ላይ የተነገረ ጥፋት

[13]እጁን በሰሜን ላይ ይዘረጋል፤
አሦርንም ያጠፋል፤
ነነዌን ፍጹም ባድማ፣
እንደ ምድረ በዳም ደረቅ ያደርጋታል።
[14]የበግና የከብት መንጋዎች፣
የፍጥረት ዐይነት ሁሉ በውስጧ
ይመሰጋሉ፤
ጒጒትና ጃርት፣
በግንቦቿ ላይ ያድራሉ።
ጩኸታቸው በየመስኮቱ ያስተጋባል፤
ፍርስራሽ በየደጃፉ ይከመራል፤
ከዝግባ የተሠሩ ተሸካሚዎችም
ይገለባሉ።
[15]ተዘልላ የኖረች፣
ደስተኛዪቱ ከተማ ይህች ናት፤
እርሷም በልቧ፣
"እኔ ብቻ ነኝ፤ ከእኔ በቀር ማንም የለም"
ያለች፣
ታዲያ እንዴት የዱር አራዊት
የሚመሰጉባት፣
ባድማ ሆና ቀረች?
በአጠገቧ የሚያልፉ ሁሉ፣
ያፌዙባታል፤ እጃቸውንም በንቀት
ያወዛውዙባታል።

## የኢየሩሳሌም የወደፊት ዕጣ

**3** ለዐመፀኛዪቱና ለረከሰች፣
ለጨቋኞች ከተማ ወዮላት!
[2]እርሷ ለማንም አትታዘዝም፤
የማንንም ዕርምት አትቀበልም፤
በእግዚአብሔር አትታመንም፤
ወደ አምላኳም አትቀርብም።
[3]ሹሞቿ የሚያገሡ አንበሶች፣
ገዦቿ ለነጋ የማይሉ፣
የምሽት ተኵላዎች ናቸው።
[4]ነቢያቷ ትዕቢተኞች፣
አታላዮችም ናቸው፤
ካህናቷ መቅደሱን ያረክሳሉ፣
በሕግም ላይ ያምፃሉ።
[5]በእርሷ ውስጥ ያለው እግዚአብሔር ጻድቅ
ነው፤
ፈጽሞ አይሳሳትም፤
በየማለዳው ቅን ፍርድ ይሰጣል፤
በየቀኑም አይደክምም፤
ዐመፀኞች ግን ዕፍረት አያውቁም።

2፥9 ዘዳ23፥6፤ 29፥23፤2ነገ19፥31፤ ኢሳ11፥14፤13፥19፤ 15፥1-16፥14፤ኤር 48፥147፤49፥16፡18፤ ሕዝ25፥17፡8-11፤ አሞ2፥13
2፥10 ኢዮ40፥12፤ መዝ9፥6፤ኢ ሳ16፥6፤ኤር48፥27
2፥11 1ዜና19፥1፤ መዝ86፥9፤ኢሳ 12፥4፤ሕዝ25፥67፤ ኢል2፥11፤ሶፎ 1፥4፤3፥9
2፥12 ዘፍ10፥6፤ ኢሳ20፥4፤ኤር46፥10
2፥13 ዘፍ10፥11፤ ኢሳ10፥5፤ሚክ5፥6፤ ናሆ1፥1፤ዘካ10፥11
2፥14 መዝ102፥6፤ ኢሳ5፥17፤14፥23፤ ራእ18፥2
2፥15 ኢሳ28፥22፤ 32፥9፤47፥8፤ኤር 49፥33፤ሕዝ27፥36፤ 28፥2፤ናሆ3፥19
3፥1 ዘዳ21፥18፤ ኤር6፥6፤ሕዝ23፥30
3፥2 ዘሌ26፥23፤ ዘዳ1፥32፤መዝ73፥28፤ ኤር7፥28፤22፥21
3፥3 ዘፍ49፥27፤ መዝ22፥13፤ሚክ3፥3
3፥4 መዝ25፥3፤ ኢሳ48፥8፤ኤር3፥20፤ 9፥4፤23፥11፤ሕዝ 22፥26፤ሚል2፥10
3፥5 ዘዳ32፥4፤ዕዝ 9፥15፤መዝ5፥3፤ኤር 3፥3፤ሰቆ3፥23፤ሕዝ 18፥25

1፥13 ማብ ይመ። አሞንና ሞዓብ በእስራኤል ላይ ምን ያህል ጥላቻ እንደነበራቸው ለማስተዋል አሞ 1፥13-15፤ 2፥1-3 ይመ። የእስራኤልን ምድር ለመያዝ ብዙ ጊዜ ተገዳድረው ነበር (መሳ 11፥12-13፤ ሕዝ 25፥3-6 ይመ)።

2፥9 *ሰዶም..ገሞራ፤* ዘፍ 19 ይመ። እነዚህ ከተሞች በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት የእግዚአብሔር የቅጣት ፍርድ አምሳያ በመሆን በዚህ ክፍል መጠቀሳቸው (ዘዳ 29፥23፤ ኢሳ 13፥19፤ ኤር 49፥18 ይመ)፤ ነቢዩ የጌታን ቀን አስፈሪነት አጒልቶ እንዲገልጽ ረድቶታል። *ዐረም፤* የአገሪቱ ሕዝብ ተግዞ ወደ ሌላ አገር መወሰዱን ያመለክታል፤ (ኢሳ 7፥23-25 ይመ)። *የተረፉትም ምድራቸውን ይወርሳሉ፤* የቊ 7 ማብ ይመ።

2፥10 *ከትዕቢታቸው የተነሣ... ሰድበው ዘብተውበታልና፤* ታማኝ የሆኑት የእግዚአብሔር ሕዝብ ቅሬታዎች አጸፋውን በመመለስ፣ የአሞናውያንንና የሞዓባውያንን ምድር የራሳቸው ያደርጋሉ።

2፥11 *ሕዝቦች... ለእርሱ ይሰግዳሉ፤* 3፥9 እና ማብ ይመ።

2፥12 *እናንተም፤* ነቢዩ ያሳንዳች ተጨማሪ ማብራሪያ በግብፅ ላይ ሊመጣ ያለውን የእግዚአብሔርን ፍርድ ያስታውቃል (ቊ 5 እና ማብ ይመ)። *በሰይፌ፤* ባቢሎንን ያመላክታል።

2፥13 *በሰሜን፤* ነነዌ ከይሁዳ በስተ ምሥራቅ የምትገኝ ብትሆንም እንኳ፣ የአሦር ሰራዊት በመጀመሪያ ወደ ምዕራብ በመጓዝ በኤፍራጥስ አድርጎ ከነዓንን ወሮአል። *ነነዌን፤* ትንቢተ ዮናስንና ትንቢተ ናሆምን ይመ። ነነዌ በ612 ዓ.ቅ.ክ. ጠፍታ ስለ ነበር፣ የሶፎንያስ አገልግሎት ከዚህ ዘመን በፊት መሆን አለበት። *ባድማ፤* ከቅርብ ዓመታት ወዲህ በተደረገው የሥነ ቅርስ ቊፋሮ መሠረት፣ ነነዌ የነበረችበት ስፍራ እንኳን አልተገኘም።

2፥15 *እኔ ብቻ ነኝ፤ ከእኔ በቀር ማንም የለም፤* ኢሳ 47፥10 ይመ፤ የአሦር ከእኔ ወዲያ ማን አለ ባይነት በትክክል ተገቢ የሚሆነው ለእግዚአብሔር ብቻ ነው (ኢሳ 45፥5-6:18:21 ይመ)። *ሆና ቀረች፤* በነነዌ ላይ ሊመጣ ያለውን ውድመት ከወዲሁ ያመለክታል።

3፥1-7 *ለጨቋኞች ከተማ ወዮላት፤* ሶፎንያስ ሌሎቹን ሕዝብ ካወገዘ በኋላ፣ ወደ ኢየሩሳሌምና ወደ እግዚአብሔር ሕዝብ ኀጢአት ፊቱን ይመልሳል፤ እግዚአብሔርንና ሕጉን የሚቃወሙ ሆነው ተገኝተዋልና። የሥነ ምግባር ብልሹነት ኅብረተ ሰቡን ከላይ እስከ ታች አዳሽቆታል፤ በየትኛውም ቦታ የሚኖሩ ሰዎች እውነተኞችን የእግዚአብሔር ነቢያት መስማት አልፈለጉም።

3፥1 *ከተማ፤* እምነቷን የተወች ኢየሩሳሌም ስለ ኀጢአቷ ተወግዛለች። *የጨቋኞች፤* ኤር 22፥3 ይመ።

3፥3-4 *ሹሞቿ ... ገዦቿ ... ነቢያቷ... ካህናቷ፤* በየትኛውም የሥራ ኀላፊነት ላይ ተመድበው የነበሩት የአይሁድ መሪዎች፣ ከተሰጣቸው ኀላፊነትና ተግባር ጋር በሚጻረር ልማድ በመጠመዳቸው ዘግናኝ ቅጣት ደርሶባቸዋል (ኤር 1፥18 እና ማብ ይመ)።

3፥3 *የሚያገሡ አንበሶች...የምሽት ተኵላዎች፤* በሥልጣን ላይ የሚገኙት በቃኝን የማያውቁ ዘራፊዎች ናቸው።

3፥4 *ትዕቢተኞች፣ አታላዮችም፤* የእግዚአብሔር ነቢያት መሆናቸውን ይፋ ቢያደርጉም የሚናገሩት ሁሉ ግን ሐሰት ነው (ኤር 5፥31፤ 14፥14፤ 23፥16:32 ይመ)። *ካህናቷ...በሕግም ላይ ያምፃሉ፤* የሕግ መምህራን መሆን ሲገባቸው ለማለት ነው (ዘዳ 31፥9-13፤ 2ዜና 17፥8-9፤ 19፥8፤ ዕዝ 7፥6፤ ኤር 2፥8፤ 18፥18፤ ሚል 2፥7 ይመ)።

⁶"ሕዝቦችን አጥፍቻለሁ፤
ምሽጋቸው ተደምስሶአል፤
ማንም እንዳያልፍባቸው፣
መንገዳቸውን ባድማ አደረግሁ፤
ከተሞቻቸው ተደምስሰዋል፤
አንድም ሰው የለም፤ ነዋሪም ከቶ
አይገኝባቸውም።
⁷እኔም ከተማዪቱን፣
'በእርግጥ ትፈሪኛለሽ፤
ዕርምትም ትቀበያለሽ' አልኳት፤
ስለዚህ መኖሪያዋ አይጠፋም፤
ቅጣቴም ሁሉ በእርሷ ላይ አይደርስም።
እነርሱ ግን በሚያደርጉት ሁሉ፣
ክፋትንም በመፈጸም እየተጉ ሄዱ።
⁸*እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤
"ስለዚህ እስክምፈርድበት[m] ቀን ድረስ
ጠብቁኝ፤
አሕዛብን ላከማች፣
መንግሥታትን ልሰበስብ፣
መዓቴንና ጽኑ ቍጣዬን፣
በላያቸው ላፈስ ወስኛለሁ፤
በቅናቴ ቍጣ እሳት፣
መላዋ ምድር ትቃጠላለችና።
⁹"በዚያ ጊዜ ሰዎች ሁሉ *የእግዚአብሔርን*
ስም እንዲጠሩ፣
ተስማምተው እንዲያገለግሉት፣
አንደበታቸውን አጠራለሁ።
¹⁰ከኢትዮጵያ ወንዞች ማዶ፣
የሚያመልኩኝ፣ የተበተኑት ሕዝቤ
ቍርባን ያመጡልኛል።
¹¹በእኔ ላይ ከፈጸማችሁት በደል ሁሉ
የተነሣ፣
በዚያ ቀን አታፍሩም፤
በትዕቢታቸው የሚደሰቱትን፣
ከዚህች ከተማ አስወግዳለሁና፤
ከእንግዲህ ወዲያ፣
በቅዱስ ተራራዬ ላይ አትታበዩብኝም።
¹²*በእግዚአብሔር* ስም የሚታመኑትን፣
የዋሃንንና ትሑታንን፤
በመካከላችሁ አስቀራለሁ።
¹³የእስራኤል ትሩፋን ኀጢአት
አይሠሩም፤
ሐሰትም አይናገሩም፤
በአንደበታቸውም ተንኰል አይገኝም።
ይበላሉ፤ ይተኛሉ፤
የሚያስፈራቸውም የለም።
¹⁴የጽዮን ልጅ ሆይ፤ ዘምሪ፤
እስራኤል ሆይ፤ እልል በይ፤
የኢየሩሳሌም ልጅ ሆይ፤
በፍጹም ልብሽ ደስ ይበልሽ፤ ሐሤትም
አድርጊ።
¹⁵*እግዚአብሔር* ቅጣትሽን አስወግዶታል፤
ጠላቶችሽን ከአንቺ መልሶአል፤
የእስራኤል ንጉሥ *እግዚአብሔር* ከአንቺ
ጋር ነው፤
ከእንግዲህ ወዲያ አንዳች ክፉ ነገር
አትፈሪም።
¹⁶በዚያ ቀን ኢየሩሳሌምን እንዲህ
ይሏታል፤
"ጽዮን ሆይ፤ አትፍሪ፤
እጆችሽም አይዛሉ።
¹⁷አምላክሽ *እግዚአብሔር* ከአንቺ ጋር ነው፤
እርሱ የሚታደግ ኀያል ነው፤
በአንቺ እጅግ ደስ ይለዋል፤
በፍቅሩ ያሳርፍሻል፤
በዝማሬም በአንቺ ሐሤት ያደርጋል።"
¹⁸"ለታወቁ ክብረ በዓላት ሐዘንን፣
ከአንቺ አስወግዳለሁ፤
ሸክምና ነቀፌታ ሆነውብሻል።[n]
¹⁹በዚያ ጊዜ፣
ያስጨነቁሽን ሁሉ እቀጣለሁ፤
አንካሶችን እታደጋለሁ፤

3፥6 ዘሌ26፥31
3፥7 ኤር7፥28፤ ሆሴ9፥9
3፥8 መዝ27፥14፤ 79፥6፤ኢሳ2፥3፤ ኤር10፥25፤ሰቆ4፥11፤ ኢዩ3፥11፤ሶፎ1፥18
3፥9 ዘፍ4፥26፤ኢሳ 19፥18፤ሶፎ2፥11
3፥10 ዘፍ10፥6፤ 2ዜና32፥23፤መዝ 68፥31፤ኢሳ60፥7
3፥11 ዘፍ50፥15፤ ዘፀ15፥17፤ዘሌ26፥19፤ መዝ59፥12፤ኢሳ 29፥22፤ኢዩ2፥26-27
3፥12 ኢሳ14፥32፤ ኤር29፥12፤ናሆ1፥7
3፥13 ዘሌ26፥6፤ ኢዮ16፥17፤መዝ 119፥3፤ኢሳ4፥3፤ 10፥21፤ኤር33፥16፤ ሕዝ34፥15፡25-28፤ ሶፎ2፥7፤ ራእ14፥5
3፥14 መዝ9፥2፡ 14፤95፥1፤ኢሳ 12፥6፤51፥11፤ ዘካ2፥10
3፥15 ኢሳ54፥14፤ ሕዝ37፥2628፤ዘካ9፥9
3፥16 2ነገ19፥26፤ ኢዮ4፥3፤ኢሳ35፥34፤ ዕብ12፥12
3፥17 ዘዳ28፥63፤ ኢሳ40፥1፤62፥4፤ 63፥1፤ሆሴ14፥4፤ ኢዩ2፥21
3፥19 ኢሳ14፥2፤ 60፥18፤ሕዝ34፥16፤ ሚክ4፥6

[m] 8 የሰባ ሊቃናቱና የሱርስቱ ቅጅ ከዚህ ጋር ይስማማሉ፤ የዕብራይስጡ ትርጉም ግን *ለመበዝበዝ እስከምነሣበት ቀን ድረስ* ይላል።
[n] 18 ወይም *በበዓል ቀን የሚያዝኑትን አሰበስብልሻለሁ፤ ሐፍረትሽ ሸክም ሆኖብኛል*

*3፥6-8፤* ኢየሩሳሌም ንስሓ ለመግባት እምቢተኛ መሆኗን ያመለክታል (2፥1-3 ማብ ይመ)።

3፥6 *ሕዝቦችን አጥፍቻለሁ፤* የሌሎች ሕዝቦች መጥፋት ለሥርዓተ አልበኛዋ ይሁዳ ትምህርት እንዲሆናት ነበር፤ ግን ፋይዳ ቢስ ሆኖ ቀረ (ቍ 7 ተመ)።

3፥7 *ክፋትንም በመፈጸም እየተጉ፤* ኤር 7፥13:25-26 ይመ።

3፥8 *ጠብቁኝ፤* አስፈሪ አደጋ እንደሚደርስባት ለይሁዳ የተነገረ ምፀት ነው። *እስክምፈርድበት፤* ክስ ከተመሠረተ በኋላ (መዝ 50፥7 ይመ)፣ ወደ ፍርድ ፍጻሜ ለመድረስ ነው። *ወስኛለሁ፤* እዚህ ላይ ጌታ የልቡን ሐሳብ በግልጽ በመናገር፣ የፍርዱን ፍጻሜ ያጠቃልላል።

*3፥9-20፤* ከእግዚአብሔር ፍርድ በኋላ የሚመጣውን መጐብኘት የሚያመለክት ባለ ሦስት አንጓ ንግግር ነው(ቍ 9-13:14-17:18-20)።

*3፥9-13፤* ጌታ ሕዝቦች እንደሚቀደሱ፣ ተበትነው የነበሩ የሕዝቡ ቅሬታዎች ወደ ምድራቸው እንደሚመለሱና ኢየሩሳሌምም ከእድፏ እንደምትነጻ ማረጋገጫ ይሰጣል።

*3፥9፤* እግዚአብሔር በሕዝቦች ላይ የሚያመጣው አስፈሪ ፍርድ መቀደሳቸውን ያስገኛል፤ ይኸውም ስሙን በመጥራት እንዲያገለግሉት ነው። የእስራኤል አምላክ በሕዝቦች ዘንድ ይመለካል፤ የእግዚአብሔርም ሕዝብ በሌሎች ሕዝቦች ዘንድ የተከበረ ይሆናል (ከቍ 19-20 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥10 *ከኢትዮጲያ፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። በእጅጉ ተበታትኖ የነበረው እንደሚሰበሰብ ያመለክታል። *ቍርባን ያመጡልኛል፤* ለበአልና ለሚልኮም ከማምጣት ይልቅ ማለት ነው (ከ1፥4-5 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥11 *በቅዱስ ተራራዬ፤* የጽዮንን ተራራ ለማለት ነው (መዝ 2፥6 ይመ)።

3፥13 *የሚያስፈራቸውም የለም፤* ከሚክ 4፥4፣ ቃል በቃል የተጠቀሰ ነው።

*3፥14-17፤* ኢየሩሳሌም ተመልሳ በቦታዋ ላይ በምትተከልበት ጊዜ (ይህም ሁለት መልክ አለው፤ ቍ 14-15 እና ቍ 16-17 ይመ)፣ ታላቅ ደስታ እንደሚሆን ነቢዩ በድጋሚ ያረጋግጣል (ከ1፥10-13 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥14 *የጽዮን ልጅ...የኢየሩሳሌም ልጅ፤* ኢየሩሳሌምና ነዋሪዎቿ በሰውኛ ዘይቤ ተገልጸዋል።

3፥15 *ጠላቶችሽን፤* በእስራኤል ላይ የተሰለፉት ሁሉ ናቸው። *የእስራኤል ንጉሥ እግዚአብሔር፤* ኢሳ 44፥6 እንዲሁም በዳዊት መዝሙር መግቢያ ላይ "ትምህርተ መለኮት" የሚለውን ይመ።

3፥16 *እጆችሽም አይዛሉ፤* ተስፋ አትቁረጭ እንደ ማለት ነው።

*3፥18-20፤* እግዚአብሔር ጽዮንን ዳግመኛ እንደሚጐበኛት የሚያረጋግጥ ማጠቃለያ ሐሳብ ነው።

3፥18፤ *ለታወቁ በዓላት፤* ዘሌ 23 ይመ።

የተበተኑትንም እሰበስባለሁ፤
በተዋረዱበት ምድር ሁሉ፣
ለውዳሴና ለክብር አደርጋቸዋለሁ።
[20]በዚያን ጊዜ እሰበስባችኋለሁ፤
ያን ጊዜ ወደ አገራችሁ
እመልሳችኋለሁ፤

3፥20 ዘዳ26፥19፤ ኢሳ56፥5፤60፥18፤ 66፥22፤ኤር29፥14፤ ሕዝ37፥12፤ኢዩ3፥1

ዐይናችሁ እያየ፣
ምርኮአችሁን በምመልስበት ጊዜ፣
መከበርንና መወደስን፣
በምድር ሕዝብ ሁሉ መካከል
እሰጣችኋለሁ"፤
ይላል እግዚአብሔር።

3፥20 *መከበርንና መወደስን ... እሰጣችኋለሁ፤* ዘዳ 12፥2-3 ይመ።

# ትንቢተ ሐጌ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ሐጌ ከዘካርያስ ጋር በመሆን ከምርኮ የተመለሱትን ሰዎች፣ ቤተ መቅደሱን እንደ ገና እንዲሠሩት ያበረታታ ነቢይ ነበር (ዕዝ 5፥1-2፤ 6፥14 ይመ)። ሐጌ ማለት "በዓል" ማለት ሲሆን፣ ይህም ነቢዩ ከሦስቱ በዓላት በአንዱ ማለትም በቂጣ በዓል፣ በሰባቱ ሱባኤ በዓልና በዳስ በዓል ጊዜ መወለዱን ያመለክታል (ከዘጸ 16፥16 ጋር ያነጻጽሩ)። በ2፥3 (ማብ ይመ) ላይ በተጠቀሰው መሠረት ይመ። ሐጌ ስለ ሰሎሞን ቤተ መቅደስ መደምሰስ ተናግሮ ይሆናል። ይህ ከሆነ ሐጌ በሚያገለግልበት ጊዜ ዕድሜው ገና ሰባ ቤት መግባቱን ያመለክታል።

### ታሪካዊ ዳራው

በ538 ዓ.ቅ.ክ ባቢሎንን ድል ያደረገው የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ፣ አይሁድ ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመለሱና ቤተ መቅደሱን እንደ ገና እንዲሠሩ የሚፈቅድ ትእዛዝ አወጣ (ዕዝ 1፥2-4፤ 6፥3-5 ይመ)። በዘሩባቤል መሪነት (ከ ዕዝ 1፥8 ማብራሪያ 'ሰሳብሳር' የሚለውን ይመ) ወደ አገራቸው የተመለሱ አምሳ ሺህ ያህል አይሁድ ቤተ መቅደሱን መሥራት ጀመሩ። ከሁለት ዓመትም በኋላ (536 ዓ.ቅ.ክ)፣ የቤተ መቅደሱን መሠረት ሠርተው ጨረሱ፤ ታላቅ ደስታም ሆነ (ዕዝ 3፥8-10)። በእድገት ላይ በነበረችው የአይሁድ ግዛት ውስጥ እንዲህ ዓይነት ድል መገኘቱም፣ የቤተ መቅደሱ መሠራት የሚያስከትለውን ፓለቲካዊና ሃይማኖታዊ ተጽእኖ የሚፈሩትን ሳምራውያንንና ሌሎች ጎረቤቶችን ቀሰቀሰባቸው እነዚህ ሕዝቦች የቤተ መቅደሱን ሥራ አጥብቀው ተቃወሙ፤ ታላቁ ዳርዮስ የፋርስ ንጉሥ እስከሆነበት እስከ 522 ዓ.ቅ.ክ ድረስ ሥራውን ለማስተጓጐል ቻሉ (ዕዝ 4፥1-5:24)።

ዳርዮስ በግዛቱ ውስጥ የሚገኙትን የተለያዩ ሃይማኖቶች ይወድ ነበር፤ እርሱ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት በ520 ዓ.ቅ.ክ ሐጌ እና ዘካርያስ መስበክ ጀመሩ (1፥1፤ ዘካ 1፥1 ይመ)። አይሁድ ከስንፍናቸው የተነሣ ከጠላቶቻቸው ይልቅ ሊወቀሱ ይገባቸው ነበር፤ ሐጌም ከዳተኝነታቸው እንዲላቀቁ ሊቀሰቅሳቸው ሞክሯል። በኤፍራጥስ ማዶ የነበረው አስተዳዳሪና ሌሎች አለቆች ቤተ መቅደሱን መልሶ ለመገንባት የሚደረገውን ጥረት ለማደናቀፍ በሞከሩ ጊዜ፣ ዳርዮስ ሙሉ በሙሉ አይሁድን ደግፎ ቆመ (ዕዝ 5፥3-6፤ 6፥6-12)። በ516 ዓ.ቅ.ክ የቤተ መቅደሱ ሥራ ተጠናቆ ለእግዚአብሔርም አገልግሎት ተለየ (ዕዝ 6፥15-18)።

### የተጻፈበት ጊዜ

የሐጌ መልእክት የተነገረው በ520 ዓ.ቅ.ክ. በአራት ወር ጊዜ ውስጥ ሲሆን፣ ይህም ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት ነው። የመጀመሪያው መልእክት የተነገረው በስድስተኛው ወር ከወሩም በመጀመሪያው ቀን ሲሆን፣ የመጨረሻው ደግሞ በዘጠነኛው ወር ከወሩም በሃያ አራተኛው ቀን ነበር፤ (የ1፥1፤ 2፥1:10 ማብ ይመ)፤ እንዲሁም ከዘካርያስ መግቢያ« የተጻፈበት ቀን» የሚለውን ይመ።

### መሪ ሐሳቡና አስተምህሮው

በብሉይ ኪዳን ውስጥ ከአብድዩ ቀጥሎ አጭሩ መጽሐፍ ሐጌ ነው፤ ቢሆንም የሚሰጠው ትምህርት ክብደት ያለው ነው። ትንቢተ ሐጌ ያለመታዘዝ (1፥6:11፤ 2፥16-17) እንዲሁም መታዘዝ (2፥7-9:19) የሚያስከትለው ውጤት ምን እንደ ሆነ በግልጽ ያመለክታል። ሕዝቡ ለእግዚአብሔርና ለቤቱ ቅድሚያ በሚሰጡበት ጊዜ ይባረካሉ እንጂ አይረገሙም። ለሚታዘዙትም የእግዚአብሔር መንፈስ መጽናናትን ብርታትን ይሰጣል (2፥4-5)።

በም2 ላይ "በሕዝቦች ሁሉ የተመረጠ" ስለ ተባለው (ቍ 7 ማብ ይመ) ስለ መሲሑ መምጣት ይናገራል ። እርሱም ሲመጣ እንደ ገና የተሠራውን ቤተ መቅደስ በክብር ይሞላል (2፥9 እንዲሁም ማብ ይመ)። መሲሑ የሚመጣ ለመሆኑም ማረጋገጫ ይሆን ዘንድ እግዚአብሔር ዘሩባቤልን የቀለበቱ ማኅተም አደረገው (2፥23 እና ማብ ይመ)። ይህ ክፍል በክርስቶስ ዳግም ምጽአት ጊዜ በአሕዛብ ላይ ከሚፈጸመው ፍርድ ጋር የተያያዘ ነው፤ በዚያን ጊዜ ሕዝቦች ይናወጣሉ፤ መንግሥታትም ይገለበጣሉ (2፥6-7 :21-22 እና ማብ ይመ፤ ከዕብ 12፥25-29 ጋር ያነጻጽሩ)።

### ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያቱ

ልክ እንደ ሚልክያስ፣ ሐጌም ዋና ሐሳቦችን ለማጕላት ብዙ ጥያቄዎችን ተጠቅሞአል (1፥4:9፤ 2፥3:19 ይመ)፤ ውጤታማ የድግግሞሽ ስልትንም ተጠቅሞአል፤ ለምሳሌ፣ "እስቲ የሠራችሁትን አስቡ" (1፥5:7፤2፥15:18) "እኔ ከእናንተ ጋር ነኝ" (1፥13፤ 2፥4) እንደዚሁም "ሰማይንና ምድርን... አናውጣለሁ" (2፥6:21) የእግዚአብሔር ቃል ወደ ሐጌ ወይም በሐጌ አማካይነት የመጣባቸው ቀናት (1፥1፤2፥1፤10:20)። የመጽሐፉን ዋና ዋና ክፍሎች ያመለክታሉ።

ብዙ ጊዜ ሐጌ በሌሎች ቅዱሳት መጻሕፍት ውስጥ የተጠቀሱትን ሐሳቦች በመድገም የሚናገር ይመስላል (1፥6ን ከዘዳ 28፥38-39፤ 2፥17ን ከዘዳ 28፥22 ጋር ያነጻጽሩ) በ2፥4 (ማብ ይመ) ላይ ሦስት

ጊዜ የተጠቀሰው፣ "በርታ" የሚለው ቃል በኢሱ 1፥6-7፡9፡18 ላይ ከተጠቀሰው የማበረታቻ ቃል ጋር ይመሳሰላል።

**አስተዋፅኦ**

1 የመጀመሪያው መልእክት ቤተ መቅደሱን መልሶ ለመሥራት የተደረገ ጥሪ (1፥1-11)
   ሀ. የሕዝቡ ሰንካላ ምክንያት (1፥1-4)
   ለ.. የሕዝቡ ድኽነት (1፥5-6)
   ሐ. እግዚአብሔር እነርሱን የረገመበት ምክንያት (1፥7-11)
2 ዘሩባቤልና ሕዝቡ የሰጡት ምላሽ (1፥12-15)
   ሀ. የመሪዎቹና የቅሬታዎቹ መታዘዝ (1፥12)
   ለ እግዚአብሔር ሠራተኞቹን ማበረታታቱ (1፥13-15)
3 ሁለተኛ መልእክት የእግዚአብሔር ክብር ቤተ መቅደሱን መሙላቱ (2፥1-9)
   ሀ. ሕዝቡ ተበረታታ (2፥1-5)
   ለ .ስለ ክብርና ስለ ሰላም የተሰጠ ተስፋ (2፥6-9)
4 ሦስተኛ መልእክት የረከሱት ሰዎች መቀደስና መባረክ (2፥10-19)
   ሀ. የኀጢአት ፈጥኖ መዛመት (2፥10-14)
   ለ. ካለመታዘዝ የተነሣ የዕርሻው ምርት መቀነሱ (2፥15-17)
   ሐ. ከቤተ መቅደሱ እንደ ገና መሠራት ጋር የሚመጣ በረከት (2፥18-19)
5 አራተኛ መልእክት ለዘሩባቤል የተሰጠው ተስፋ (2፥20-23)
   ሀ. በሕዝቦች ላይ የሚደርስ ፍርድ (2፥20-22)
   ለ. የዘሩባቤል መመረጥ (2፥23)

## የእግዚአብሔርን ቤት ለመሥራት የተደረገ ጥሪ

**1** ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት፣ በስድስተኛው ወር የመጀመሪያ ቀን፣ የእግዚአብሔር ቃል በነቢዩ በሐጌ በኩል ወደ ይሁዳ ገዥ ወደ ሰላትያል ልጅ ወደ ዘሩባቤልና ወደ ሊቀ ካህናቱ ወደ ኢዮሴዴቅ ልጅ ወደ ኢያሱ[ሀ] እንዲህ ሲል መጣ፤

[2] *እግዚአብሔር* ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ "ይህ ሕዝብ፣ '*የእግዚአብሔር* ቤት የሚሠራበት ጊዜ ገና ነው' ይላል።"

[3] *የእግዚአብሔርም* ቃል በነቢዩ በሐጌ በኩል እንዲህ ሲል መጣ፤ [4] "ይህ ቤት ፈርሶ ሳለ፣ እናንተ ራሳችሁ በተዋቡ ቤቶቻችሁ ውስጥ ለመኖር ጊዜው ነውን?"

[5] ስለዚህ *እግዚአብሔር* ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ "እስቲ የሠራችሁትን አስቡ፤ [6] ብዙ ዘራችሁ፤ ነገር ግን ያጨዳችሁት ጥቂት ነው፤ በላችሁ፤ ግን አልጠገባችሁም፤ ጠጣችሁ፤ ግን አልረካችሁም፤ ለበሳችሁ፤ ግን አልሞቃችሁም፤ ደመወዝን ተቀበላችሁ፤ ግን በቀዳዳ ኰረጆ የማስቀመጥ ያህል ነው።"

[7] *እግዚአብሔር* ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ "እስቲ የሠራችሁትን አስቡ፤ [8] ወደ ተራራ ውጡ፤ ዕንጨት አምጡ፤ ቤቱን ሥሩ፤ እኔም በእርሱ ደስ ይለኛል፤ እከበርበታለሁም" ይላል *እግዚአብሔር*። [9] ሁሉን የሚገዛ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ "ብዙ ተስፋ አደረጋችሁ፤ ያገኛችሁት ግን ጥቂት ነው፤ ወደ ቤት ያስገባችሁትንም እኔ እፍ አልሁበት፤ ይህ የሆነው ለምን ይመስላችኋል? የእኔ ቤት ፈርሶ እያለ ሁላችሁም የራሳችሁን ቤት ለመሥራት ስለምትሮጡ ነው፤ [10] ስለዚህ በእናንተ ምክንያት ሰማያት ጠል ከለከሉ፤ ምድርም ፍሬዋን ነሣች። [11] እኔም በዕርሻዎችና በተራሮች፣ በእህሉና በአዲሱ ወይን ጠጅ፣ በዘይቱና ምድር በምታፈራው ሁሉ፣ በሰውና በእንስሳ፣ በእጃችሁም ሥራ ላይ ድርቅ አመጣሁ።"

[12] ከዚህ በኋላ የሰላትያል ልጅ ዘሩባቤል፣ ሊቀ ካህናቱ የኢዮሴዴቅ ልጅ ኢያሱ፣ ከምርኮ የተረፉትም ሕዝብ የአምላካቸውን *የእግዚአብሔርን* ድምፅ፣ የነቢዩንም የሐጌን መልእክት ሰሙ፤ አምላካቸው *እግዚአብሔር* ልኮታልና። ሕዝቡም *እግዚአብሔርን* ፈሩ።

[13] ቀጥሎም *የእግዚአብሔር* መልእክተኛ ሐጌ፣ ይህን የእግዚአብሔርን መልእክት ለሕዝቡ እንዲህ ሲል ተናገረ፤ "እኔ ከእናንተ ጋር ነኝ" ይላል *እግዚአብሔር*። [14] ስለዚህ *እግዚአብሔር* የይሁዳን ገዥ፣ የሰላትያልን ልጅ የዘሩባቤልን መንፈስ፣ የሊቀ ካህናቱን የኢዮሴዴቅን ልጅ፣ የኢያሱን መንፈስና፣ ከምርኮ የተረፈውን ሕዝብ ሁሉ መንፈስ አነሣሣ፤ እነርሱም መጥተው የአምላካቸውን *የእግዚአብሔር* ጸባኦት ቤት መሥራት ጀመሩ። [15] ይህም የሆነውም ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት፣ በስድስተኛው ወር፣ በሃያ አራተኛው ቀን ነበር።

1፥1 1ዜና3፥19፤ 6፥15፤ዕዝ2፥2፤ 3፥2፤4፥24፤5፥1፤5፥3፤ ነህ5፥14፤ዘካ3፥8፤ ማቴ1፥12-13
1፥2 ዕዝ1፥2፤ ኢሳ13፥14፤29፥13
1፥3 ዕዝ5፥1
1፥4 ቍ9፤2ሳሙ7፥2፤ ኤር33፥12
1፥5 ቍ7፤ሰቆ3፥40፤ ሐጌ2፥15፡18
1፥6 ዘሌ26፥20፤ ኢሳ5፥10፤9፥20፤ 55፥2፤አሞ4፥8፤ ሐጌ2፥16፤ዘካ8፥10
1፥7 ቍ5
1፥8 ዘፀ29፥43፤ 1ዜና14፥1፤ኢዮ22፥3፤ መዝ132፥13-14፤ ኤር13፥11
1፥9 ቍ 4፤ ዘዳ28-38፤ ነህ13፥11፤መዝ103፥16፤ ኢሳ5፥10፤ሕዝ22፥21
1፥10 ዘፍ27፥28፤ ዘሌ26፥19፤ዘዳ28፥23፡ 24፤1ነገ17፥1
1፥11 ዘኍ18፥12፤ ዘዳ11፥26፤28፥22፡51፤ ሩት1፥1፤1ነገ17፥1፤ መዝ4፥7፤ኢሳ5፥6፤ 7፥25፤ሐጌ2፥17
1፥12 ቍ1፡14፤ ዘዳ31፥12፤ ኢዮ36፥11፤ኢሳ1፥2፡ 9፤50፥10፤ሐጌ2፥2፤ ማቴ28፥20
1፥13 ቍ1፤ዘፍ26፥3፤ ዘኍ14፥9፤27፥21፤ 2ዜና36፥15፤ ማቴ2 8፥20፤ ሮሜ8፥31
1፥14 ቍ12፤1ዜና6፥15፤ዕዝ1፥1፡5፤5፥2
1፥15 ቍ1፤ ዕዝ4፥24፤ሐጌ2፥10፡20

[ሀ] 1 የየሹዋ ተለዋጭ ስም ሲሆን በሐጌ መጽሐፍ ውስጥ በብዛት ይገኛል።

1፥1 *ዳርዮስ በነገሠ፤* ከ522-486 ዓ.ቅ.ክ ዳርዮስ ሂይስታዕጲስ፣ ፋርስን ገዝቶ ነበር። በዛሬዪቱ ኢራን ውስጥ ቢሲቱን በሚል ስም በሚታወቀው ዐለት ላይ በሦስት የተለያዩ ቋንቋዎች የተቀረጸውን ጽሑፍ ያዘጋጀው ይኸው ንጉሥ ነው። *በሁለተኛው ዓመት በስድስተኛው ወር የመጀመሪያ ቀን፤* ነሐሴ 29 ቀን 520 ዓ.ቅ.ክ ማለት ነው። *የመጀመሪያ ቀን፤* አንዳንድ ጊዜ በወር መባቻ ሰዎች የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለማወቅ ነቢያትን ይጠይቁ ነበር (2ነገ4፥22-23 እና የኢሳ1፥14 ማብ ይመ)። *ሰላትያል፤* በ1ዜና 3፥17-19 ላይ እንደ ተጻፈው፣ ሰላትያል የዘሩባቤል አያት ነው፤ አንዳንድ ጊዜ በዕብራይስጡ የልጅ ልጅ "ልጅ" ተብሎ ይጠራል። *ዘሩባቤልና፤* በዕዝራ መጽሐፍ፣ "ሰሳብሳር" ተብሎአል፤ የዕዝ1፥8 ማብ ይመ። *ኢዮሴዴቅ፤* በናቡከደነፆር ተማርኮ ተወስዶ ነበር (1ዜና6፥15)። *ኢያሱ፤* በቍ12፡ 14፤2፥2፡4 ላይ ከዘሩባቤል ጋር፣ ይህ ስም እንደዚሁ አብሮ ተጠቅሶአል።

1፥2፤ *እግዚአብሔር ጸባኦት ፤* በሐጌ፣ በዘካርያስና በሚልክያስ መጻሕፍት ከዘጠና ጊዜ በላይ ተጠቅሶአል (የኢሳ13፥4 ማብ ይመ)። *ይህ ሕዝብ፤* 2፥14 ይመ። ከኀጢአታቸው የተነሣ ሕዝቡ "ሕዝቤ" ተብሎ አልተጠራም (ኢሳ6፥9፤8፥6፡11-12፤ኤር14፥10-11ይመ፤ እንዲሁም የሆሴ1፥9ማብ ይመ)። *ጊዜ ገና ነው፤* በ536 ዓ.ቅ.ክ ላይ (ዕዝ3፥8-10ይመ) የቤተ መቅደሱ መሠረት ከተጣለ በኋላ፣ ተቃውሞ ስለ ተነሣ እስከ 520 ዓ.ቅ.ክ ድረስ ሥራው ተቋረጠ (ዕዝ4፥1-5፡24 ይመ)።

1፥4፤ *በተዋቡ ቤቶቻችሁ፤* ልዩ ልዩ ኅብር ባላቸው የዝግባ ሳንቃዎች ያማሩ የነገሥታትን መኖሪያዎችን የሚያመለክት ነው (1ነገ7፥3፡7፤ኤር22፥4)።

1፥6 *ብዙ ዘራችሁ....ያጨዳችሁት ጥቂት ነው፤* ካለመታዘዝ የተነሣ የሚደርስ ርግማን ነው (ዘዳ28፥38-39)። እንዲሁም ምድር ከእግዚአብሔር ፍርድ የተነሣ መካን እንደምትሆን በዘሌ26፥20 ላይ ተገልጾአል። *ጠጣችሁ....አልረካችሁም፤* ከኢሳ55፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ። ሕዝቡ የሚያደርገው ሁሉ ትክክል ይሁን አይሁን (ከሆሴ4፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ኑሮው ሁሉ ከንቱ ነበር። *በቀዳዳ ኰረጆ፤* በራብ ጊዜ የሸመታው ዋጋ ባጭር ጊዜ ያሻቅባል፡

1፥8፤ *ተራራ... ዕንጨት፤* ምናልባት በኢየሩሳሌም አካባቢ ካሉት ኰረብታዎች የሚያመጡአቸው ዕንጨቶች፣ ቀደም ሲል ከሊባኖስ ተገዝተው ለመጡት የዝግባ ዕንጨቶች ተጨማሪ እንዲሆኑ ተፈልጐ ሳይሆን አይቀርም (ዕዝ3፥7 ይመ)። *በእርሱ ደስ ይለኛል፤* እዚያ በሚቀርበው መሥዋዕት ማለት ነው (ከኢሳ1፥11 ጋር ያነጻጽሩ)። *እከበርበታለሁም፤* የሚታዘዝ ሕዝብ እግዚአብሔር እንዲመሰገንና እንዲከበር ያደርጋል (ኤር13፥11 ይመ)።

1፥10 *ጠል፤* ሳያቋርጥ የሚወርድ ጠል፣ እንደ መደበኛው ዝናብ ሁሉ ጠቃሚ ነው(2ሳሙ1፥21፤1ነገ17፥1 ይመ)።

1፥11 *በተራሮች፤* በተራሮቹ ላይ በተለይ ዕርከን እየተደረገ ይታረሱ ነበር (መዝ104፥13-15፤ኢሳ7፥25፤ኢል3፥18 ይመ)። *በእህሉና በአዲሱ ወይን ጠጅ፣ በዘይቱና፤* እነዚህ ምድሪቱ የምታበቅላቸው ሦስቱ ዋና ዋና ተክሎች ናቸው፤ አብዛኛውን ጊዜ ከበረከት ወይም ከመርገም ጋር በተያያዘ ሁኔታ ተጠቅሰዋል (ዘዳ7፥13፤11፥14፤28፥51፤ ሆሴ2፥8፡22 ይመ)። የወይራ ዘይት ለምግብነት፣ ለቅባትነት ወይም ለመድኀኒትነት ያገለግል ነበር። *በሰውና በእንስሳ፤* ድርቁ ሰውንም ሆነ እንስሳትን ያጠቃል ማለት ነው።

1፥12፤ *የተረፉትም፤* የኢሳ1፥9 ማብ ይመ። *እግዚአብሔርን ፈሩ፤* እግዚአብሔርን መፍራት ልዩ አክብሮትንና ታዛዥነትን ማሳየት ማለት ነው (ዘዳ31፥12-13፤ሚል1፥6፤3፥5፡16 ይመ)።

1፥13 *መልእክተኛ፤* ለነቢያት (2ዜና36፥15፤ኢሳ42፥19 እና ማብ ይመ) ወይም ለካህናት የተሰጠ (ሚል2፥7 ይመ) የማዕረግ ስም ነው። *"እኔ ከእናንተ ጋር ነኝ"፤* በነገሮች ሁሉ ስኬታማ የመሆንን እርግጠኛነት የሚያመለክት ነው (2፥4፤ዘኍ14፥9 እንዲሁም ዘፍ26፥3 እና ማብ ይመ)።

1፥14 *መንፈስ አነሣሣ፤* በዕብራይስጡ ይህ ሐረግ፣ "ልቡን አነሣሣ" ተብሎ በዕዝ1፥5 ላይ ተጽፎአል፤ ይኸውም እግዚአብሔር ይህንኑ ሕዝብ ወደ አገሩ እንዲመለስና ቤተ መቅደሱን እንዲሠራ እንዴት እንዳነሣሣው የሚያሳይ ነው።

1፥15 *በስድስተኛው ወር፣ በሃያ አራተኛው ቀን፤* መስከረም 21 ቀን 520 ዓ.ቅ.ክ ነው።

## ቃል የተገባው የአዲሱ ቤት ክብር

**2** በሰባተኛው ወር፣ በሃያ አንደኛ ቀን የእግዚአብሔር ቃል በነቢዩ በሐጌ በኩል እንዲህ ሲል መጣ፤ [2]“ለይሁዳ ገዥ ለሰላትያል ልጅ ለዘሩባቤል፣ ለሊቀ ካህናቱ ለኢዮሴዴቅ ልጅ ለኢያሱ፣ ከምርኮ ለተረፈውም ሕዝብ እንዲህ ብለህ ተናገር፤ እንዲህም ብለህ ጠይቃቸው፤ [3]‘ይህን ቤት በቀድሞ ክብሩ ሳለ ያየ፣ ከመካከላችሁ ማን አለ? አሁንስ ምን መስሎ ይታያችኋል? ይህ በፊታችሁ ምንም እንዳይደለ የሚቈጠር አይደለምን? [4]‘እግዚአብሔር ጸባኦት እንዲህ ይላል ‘አሁን ግን ዘሩባቤል ሆይ፤ በርታ፤ የሊቀ ካህናቱ የኢዮሴዴቅ ልጅ ኢያሱ ሆይ፤ በርታ፤ እናንተም የምድሪቱ ሕዝብ ሁሉ በርቱ’ ይላል እግዚአብሔር፤ ‘እኔ ከእናንተ ጋር ነኝና ሥሩ’ ይላል ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር፤ [5]‘ከግብፅ በወጣችሁ ጊዜ የገባሁላችሁ ቃል ይህ ነው፤ መንፈሴም በመካከላችሁ ይሆናልና አትፍሩ።’

[6]“ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ ‘በቅርብ ጊዜ እንደ ገና ሰማያትንና ምድርን፣ ባሕሩንና የብሱን አንድ ጊዜ አናውጣለሁ። [7]ሕዝቦችን ሁሉ አናውጣለሁ፤ የሕዝቦችም ሀብት ሁሉ ወደዚህ ይመጣል፤ ይህንም ቤት በክብር እሞላዋለሁ’ ይላል ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር። [8]‘ብሩ የእኔ ነው፤ ወርቁም የእኔ ነው’ ይላል ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ጸባኦት፤ [9]‘የዚህ የአሁኑ ቤት ክብር ከቀድሞው ቤት ክብር ይበልጣል’ ይላል ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ጸባኦት፤ ‘በዚህም ቦታ ሰላምን እሰጣለሁ’ ይላል ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ጸባኦት።”

2፥1 ዕ10:20፤ ዘሌ23፥34፤ዕዝ5፥11 ዮሐ7፥37
2፥2 1ዜና6፥15፤ ሐጌ1፥1:12
2፥3 ዕዝ3፥12፤ ኢሳ60፥7፤ዘካ4፥10
2፥4 ዘፀ33፥14፤ ዘኍ14፥9፤2ሳሙ5፥10፤ 1ዜና6፥15፤28፥20፤ ዘካ8፥9፤ሐሥ7፥9፤ ኤፌ6፥10
2፥5 ዘፍ6፥18፤ 15፥1፤ዘፀ29፥46፤ 1ዜና28፥20፤ ዕዝ5፥2፤ነህ9፥20፤ ዘካ8፥13
2፥6 ዘፀ19፥18፤ ኢዮ9፥6፤ ኢሳ10፥25፤ 14፥16፤ሕዝ38፥19፤ ዕብ12፥26
2፥7 ዘፀ16፥7፤29፥43፤ 1ሳሙ9፥20፤ ኢሳ60፥7፤ሉቃ2፥32
2፥8 1ዜና29፥2
2፥9 ዘሌ26፥6፤ ዕዝ3፥12፤ መዝ85፥9፤ ኢሳ11፥10፤60፥7:17
2፥10 ቍ1፤ሐጌ1፥15
2፥11 ዘሌ10፥10-11፤ ዘዳ17፥8-11፤ 33፥8፤ኤር18፥18
2፥12 ዘፍ7፥2፤ ዘሌ6፥27፤ኤር11፥15፤ ማቴ23፥19

## ተግሣጽና በረከት

[10]ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት፣ በዘጠነኛው ወር፣ በሃያ አራተኛው ቀን የእግዚአብሔር ቃል በነቢዩ በሐጌ በኩል እንዲህ ሲል መጣ፤ [11]“እግዚአብሔር ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ ‘ሕጉ ምን እንደሚል ካህናቱን እንዲህ ብለህ ጠይቅ፤ [12]አንድ ሰው የተቀደሰውን ሥጋ በልብሱ ዕጥፋት ቢይዝ፣ ያም ዕጥፋት እንጀራ ወይም ወጥ፣ የወይን ጠጅ ወይም ዘይት ወይም ሌላ ምግብ ቢነካ የተቀደሰ ይሆናልን?”

ካህናቱም፣ “የተቀደሰ አይሆንም” ብለው መለሱ።

[13] ሐጌም፣ “ሬሳ በመንካቱ የረከሰ ሰው፣ ከእነዚህ አንዱን ቢነካ፣ የተነካው ነገር ይረክሳልን?” ሲል ጠየቀ።

2፥13 ዘሌ22፥4-6፤ ዘኍ19፥13

---

2፥1 *በሰባተኛው ወር፣ በሃያ አንደኛው ቀን፤* ጥቅምት 17 ቀን 520 ዓ ቅ ክ ማለት ነው፤ ይህ የዳስ በዓል የሚከበርበት ቀን ነው። የሚመረተው እህል በብዛቱም ሆነ በጥራቱ ዝቅተኛም ቢሆን እንኳ (1፥11፤ከዮሐ7፥37 ጋር ያነጻጽሩ)፣ በበጋው ወራት የመከር በዓል የሚከበርበት ጊዜ ነው። ንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደሱን መርቆ የከፈተው በዚሁ የበዓል ወቅት ነበር(1ነገ8፥2)።

2፥3 *ያየ፤* ከተማረኩት መካከል በዕድሜ የገፉትን ማለት ነው (ምናልባትም ራሱን ሐጌን ሊጨምር ይችላል)፤ እነዚህ ሰዎች ሰሎሞን የሠራውን፣ በውበቱም በታላቅነቱም የተደነቀውን፣ ከ66 ዓመት በፊት በባቢሎናውያን የተደመሰሰውን ቤተ መቅደስ በዐይናቸው ያዩትን የሚያመለክት ነው። *ይህን ቤት በቀድሞ ክብሩ፤* ቍ7 እና 9 ይመ። ዘሩባቤል የሠራው ቤተ መቅደስ፣ ሰሎሞን ከሠራው ቤተመቅደስ ቀጥሎ የተሠራ መሆኑ ይታመናል። *በፊታችሁ ምንም እንዳይደለ የሚቈጠር አይደለምን?* የቤተ መቅደሱ መሠረት በተጣለ ጊዜ ከተነሣው ተቃውሞ ጋር ያነጻጽሩ(ዕዝ3፥12)።

2፥4 *በርታ...ሥሩ፤* ሰሎሞን ቤተ መቅደሱን እንዲሠራ ለማበረታታት፣ ዳዊትም ይህን ቃል በ1ዜና28፥20 ላይ ተናግሮታል። የነነዌን ልጅ ኢያሱን በዚሁ ቃል እግዚአብሔር አበረታቶታል (ኢሱ1፥6-7:9:18)። *እኔ ከእናንተ ጋር ነኝና፤* 1፥13 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 1ዜና28፥20ይመ። ሰሎሞንን የረዳ እግዚአብሔር፤ ለዘሩባቤልና ለሕዝቡም ኀይልን ይሰጣቸዋል።

2፥5 *መንፈሴም፤* ሕዝቡን ከግብፅ ባርነት አውጥተው በምድረበዳ በመሩበት ወቅት፣ መንፈስ ቅዱስ በሙሴና በሰባው ሽማግሌዎች ላይ አድሮባቸው ነበር (ዘኍ11፥16-17:25፤ ኢሳ63፥11 ይመ)። እንዲሁም ዘካ4፥6 እና ማብ ይመ። *አትፍሩ፤* የቍ4፣ የኢሱ1፥18፣ የኢሳ 41፥10 ማብ ይመ።

2፥6 እግዚአብሔር በአሕዛብ ላይ የሚፈርድበት ቀን እንደሚመጣ የተነገረበት ነው፤ ይህም የፋርስ መንግሥት በታላቁ እስክንድር (333 –330 ዓ. ቅ. ክ.)እጅ እንደሚወድቅ የሚያሳይ ምልክት ነው። ዕብ12፥26-27 ይህንን ቍጥር፣ በክርስቶስ ዳግም ምጽአት ጊዜ በአሕዛብ ላይ ከሚፈጸመው ፍርድ ጋር ያያይዘዋል። እዚህና በቍ21-22 ላይ አሕዛብ እንደሚናወጡ የተነገረው ቃል፣ የግብፅን ጦር በቀይ ባሕር በማስጠም የተፈጸመውን ፍርድ ያስታውሳል ከኢሳ14፥16-17 ጋር ያነጻጽሩ።

2፥7 *የሕዝቦችም ሀብት ...ይመጣል፤* መሲሑ በሚመጣ ጊዜ የሚፈጸም ሊሆን ይችላል (ከሚል3፥1 ጋር ያነጻጽሩ)። “ሀብት” የሚለው ቃል ሰውን ምናልባትም መሲሑን ሊያመለክት ይችላል፤ በ1ሳሙ9፥20 እና ዳን 9፥23 ላይ ተመሳሳይ የሆነው የዕብራይስጥ ቃል ዳን 11፥37 “እጅግ የተወደድህ” የሚል ትርጒም አለው፤ የከበሩ ዕቃዎችንም ያመለክታል (2ዜና 20፥25፤ 32፥27ይመ)፣ ይኸውም ንጉሥ ዳርዮስ ለቤተ መቅደሱ እንዳበረከተው ስጦታ ማለት ነው (ዕዝ6፥8)። እንግዲህ ነገሩ ይህ ከሆነ፣ በኢሳ60፥5 ላይ የአሕዛብ ሀብት ወደ ጽዮን ይመጣል ከሚለው ጋር ተመሳሳይ ነው። *በክብር እሞላዋለሁ፤* “ክብር” የሚለው ቃል የሀብትን ትልቅነት ወይም (ኢሳ60፥7:13 እና ማብ ይመ) ህልዎተ እግዚአብሔርን የሚያመለክት ነው (ዘፀ40፥34-35፤1ነገ8፥10-11)። ክርስቶስ ወደ ምድራዊቷ ቤተ መቅደስ በመጣ ጊዜ፣ ህልዎተ እግዚአብሔር ከመቼውም ጊዜ ይልቅ ታይቶአል (ሉቃ2፥27:32)።

2፥8 *ብሩ...ወርቁም፤* እግዚአብሔር፣ ለሰሎሞን ቤተ መቅደስ (1ዜና29፥2:7) እንዲሁም ለዘሩባቤል ቤተ መቅደስ አዘጋጅቶአል (ዕዝ6፥5)።

2፥9 *ክብር...ይበልጣል፤* በመጨረሻ መሲሑ በዚያ ስለሚገኝ ነው (ቍ7 እና ማብ ይመ)። *በዚህም ቦታ፤* ምናልባት ኢየሩሳሌምን ሊሆን ይችላል (ኢሳ60፥17 እና ማብ ይመ)። *ሰላምን እሰጣለሁ፤* ምናልባት አባባሉ ቀጥታ ባልሆነ መንገድ የካህኑን ቡራኬ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ዘኍ6፥26)።

2፥10 *በዘጠነኛው ወር፣* በሃያ አራተኛው ቀን፣ ታኅሣሥ 18ቀን 520 ዓ. ቅ. ክ ማለት ነው፤ይህም የክረምት ወራት ሰብል የሚዘራበት ወቅት ነው።

2፥11 *ካህናቱን፤* የሕጉን ትክክለኛ ትርጒም እንዲናገሩ ይጠየቁ ነበር (ኤር18፥18፤ሚል2፥7-9 ይመ)።

2፥12 *የተቀደሰውን ሥጋ* ከታረደው እንስሳ ለመሥዋዕት ተለይተው የተቀመጡ ብልቶች ማለት ነው። *የተቀደሰ ይሆናልን?* ቅድስናን ማስተላለፍ ይቻላል? የሚል ጥያቄ ነው። የተቀደሰው ሥጋ ጨርቁን እንዲቀደስ አድርጎታል፤ ምክንያቱም ሥጋው በቀጥታ ጨርቁን ነክቶታል (ዘሌ6፥27 ይመ)፤ ይሁን እንጂ ጨርቁ ያን ቅድስና ወደ ሌላ ሦስተኛ ነገር ማስተላለፍ አይችልም (ሕዝ46፥20 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥13 *ይረክሳልን?* ከቅድስና ይልቅ በሥርዐቱ መሠረት መርከስ፣ ከአንዱ ወደ ሌላው በቀላሉ ይተላለፋል፤ የረከሰ ሰው የነካው ነገር ሁሉ ይረክሳል። (ዘኍ19፥11-13:22)።

ካህናቱም፣ “አዎን፣ ይረክሳል” ሲሉ መለሱ::

[14]ከዚያም ሐጌ እንዲህ አለ፤ “ ‘ይህ ሕዝብና ይህ ወገንም በፊቴ እንደዚሁ ነው’ ይላል እግዚአብሔር፤ ‘የእጃቸው ሥራና የሚያቀርቡት ሁሉ የረከሰ ነው’::

[15] “ ‘እንግዲህ ከዛሬ ጀምራችሁ በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ድንጋይ በድንጋይ ላይ ከመነባበሩ በፊት የነበረውን ሁኔታ አስተውሉ::

[16]አንድ ሰው ሃያ መስፈሪያ ወደሚሆን የእህል ክምር በመጣ ጊዜ፣ ዐሥር ብቻ አገኘ፤ አምሳ ማድጋ የወይን ጠጅ ለመቅዳት ወደ መጭመቂያው በሄደ ጊዜ፣ ሃያ ብቻ አገኘ፤ [17]የእጃችሁን ሥራ ሁሉ በዋግ፣ በአረማሞና በበረዶ መታሁት፤ እናንተ ግን ወደ እኔ አልተመለሳችሁም’ ይላል እግዚአብሔር፤ [18]‘ከዚህ ቀን ጀምሮ፣ ይኸውም ከዘጠነኛው ወር ሃያ አራተኛ ቀን ጀምሮ የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ መሠረት እስከተጣለበት ቀን ድረስ ያለውን ዘመን አስተውሉ፤ ልብ ብላችሁም አስቡ፤ [19]በጐተራ የቀረ ዘር አሁንም ይገኛልን? የወይኑና የበለሱ ዛፍ፣ የሮማኑና የወይራው ዛፍ እስካሁን አላፈሩም::

“ ‘ከዚህ ቀን ጀምሮ እባርካችኋለሁ::’ ”

2፥14 መዝ51፥17፤ ኢሳ1፥13፤ 29፥13
2፥15 ዕዝ3፥10፤ 4፥24፤ ሐጌ1፥5
2፥16 ዘዳ28፥38፤ ሩት3፥7፤ ኢዮ24፥11፤ ኢሳ5፥2፡ 10፤ ሐጌ1፥6
2፥17 ዘፀ9፥18፤ ዘዳ28፥22፤ መዝ78፥48፤ ኢሳ9፥13፤ ኤር3፥10፤ አሞ4፥6፤ ሐጌ1፥11
2፥18 ዕዝ3፥11፤ ሐጌ1፥5
2፥19 ዘፍ12፥2፤ ዘዐ28፥33፤ ዘሌ25፥21፤ መዝ128፥1-6፤ ኢል1፥12፤ 2፥14
2፥20 ቍ1፤ ዕዝ5፥11 ሐጌ1፥15
2፥21 ዕዝ5፥2፤ ኢሳ14፥16፤ ሕዝ38፥19-20
2፥22 ዘፍ19፥25፤ ዘፀ15፥21፤ መሳ7፥22፤ ኢዮ2፥13፤ ሕዝ38፥21፤ ዳን2፥44፤ ሚክ5፥10

## እግዚአብሔር ለዘሩባቤል የሰጠው ተስፋ

[20]በወሩ ሃያ አራተኛ ቀን፣ የእግዚአብሔር ቃል ዳግመኛ እንዲህ ሲል ወደ ሐጌ መጣ፤ [21]“ለይሁዳ ገዥ ለዘሩባቤል ሰማያትንና ምድርን እንደማናውጥ ንገረው፤ [22]የመንግሥታትን ዙፋን እገለብጣለሁ፤ የባዕዳንን መንግሥታት ኀይል አጠፋለሁ፤ ሠረገሎችንና ሠረገለኞችን እገለብጣለሁ፤ ፈረሶችና ጋላቢዎቻቸውም በገዛ ወንድሞቻቸው ሰይፍ ይወድቃሉ::

[23] “ ‘እግዚአብሔር ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ ‘በዚያን ቀን ባሪያዬ የሰላትያል ልጅ ዘሩባቤል ሆይ፤ እኔ እወስድሃለሁ’ ይላል እግዚአብሔር፤ ‘እንደ ማተሚያ ቀለበቴ አደርግሃለሁ፤ እኔ መርጬሃለሁና’ ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት::”

2፥23 ዘፍ38፥18፤ ዘፀ28፥9፤ ኢሳ2፥11፤ 10፥20፤ 20፥3፤ ዳን9፥24-26፤ ዘካ4፥10፤ ማቴ1፥12፤ 2ቆሮ1፥22

[a]15 ወይም ላለፉት ቀናት እንደ ማለት ነው::

2፥14 *ይህ ሕዝብና* ፤ 1፥2 እና ማብ ይመ:: *የእጃቸው ሥራና ....የረከሰ ነው፤* ምንም እንኳ ሕዝቡ ወደ ቅድስት አገር ተመልሶ ቢገባም፣ የምድሪቱ ቅድስና ሕዝቡን ሊቀድሰው አልቻለም:: ቤተ መቅደሱን መሥራት በተመለከተ እግዚአብሔርን መታዘዝ ይኖርባቸዋል (የቍ12-13ማብ ይመ)::

2፥15 *ድንጋይ.....ከመነባበሩ በፊት፤* ከስድስተኛው ወር፣ ከሃያ አራተኛው ቀን በፊት ማለት ነው (1፥15)::

2፥16 *ክምር፤* ምናልባት የእህል ክምር ሊሆን ይችላል (ኤር50፥26 ይመ):: *ዐሥር ብቻ....ሃያ ብቻ፤* መከሩ የተጠበቀውን ያህል ሊሰበሰብ ያልቻለው፣ ከሕዝቡ ኀጢአት የተነሣ እንደ ሆነ ተገልጾአል 1፥11፣ ኢሳ5፥10 እና ማብ ይመ:: *የወይን ጠጅ ....መጭመቂያው፤* የወይን ጭማቂ የሚጠራቀምበት ገንዳ ማለት ነው የኢሳ16፥10ማብ ይመ::

2፥17 *በዋግ፣ በአረማሞና፤* እነዚህ ነገሮች ባለመታዘዝ ምክንያት የሚመጡ የእርግማን ውጤት መሆናቸው በዘዳ28፥22 ላይ ተገልጾአል፤ እንዲሁም 1ነገ8፥37፤ አሞ4፥9 ይመ:: *በበረዶ፤* የግብፅን ምድርና እንስሳት እንዲያጠፋ ተልኮ ነበር (ዘፀ 9፥25፤ መዝ78፥47-48 ይመ):: *አልተመለሳችሁም፤* አሞ4፥9 ይመ::

2፥18 *መሠረት እስከ ተጣለበት ... ድረስ* በ536 ዓ.ቅ.ክ. የቤተ መቅደሱ መሠረት ሲሠራ ይህን የመሰለ ቡራኬ ተሰጥቶ ነበር (ዕዝ3፥11)፤ ይህም ዳግመኛ በኀጢያት እንዳይወድቁ የሚያስጠነቅቅ ነው::

2፥19 *የወይኑና የበለሱ ዛፍ፣ የሮማኑና የወይራው ዛፍ፤* የወይን፣ የበለስና የሮማን ፍሬ የሚደርሰው በነሐሴና በመስከረም ሲሆን፣ የወይራ ዘይት ፍሬ ደግሞ ከመስከረም እስከ ኅዳር ባለው ጊዜ ውስጥ ይደርሳል:: እነዚህም ቀደም ብሎ እንደ ተጠቀሱት የእህል ሰብሎች የተጠበቀውን ያህል ፍሬ መስጠት አልቻሉም (1፥11ማብ ይመ):: *እባርካችኋለሁ፤* ለሐጌ መልእክት ከሚሰጡት ምላሽ የተነሣ፣ የተትረፈረፈ በረከት እንደሚያገኙ ተስፋ ተሰጥቶአቸዋል፤ ከሚል 3፥10 ጋር ያነጻጽሩ::

*2፥20* የቍ10 ማብ ይመ::

2፥21 *ምድርን እንደማናውጥ፤* ቍ6ንና ማብ ይመ::

2፥22 *እገለብጣለሁ....ይወድቃሉ፤* በዕብራይስጡ ይህ ቃል የሰዶምንና የገሞራን ጥፋት ለማመልከት ጥቅም ላይ ውሉአል:: (ዘፍ19፥25፤ አሞ4፥11):: *ሠረገሎችንና..... ፈረሶችና ጋላቢዎቻቸውም፤* በቀይ ባሕር ውስጥ ከሰጠመው የፈርዖን ሰራዊት ጋር ያነጻጽሩ (ዘፀ15፥1:4:19:21):: *በገዛ ወንድሞቻቸው፤* የምድያማውያን ሰራዊት (መሳ7፥22)፣ ጎግ (ሕዝ38፥21) እንዲሁም በመጨረሻው ዘመን ኢየሩሳሌምን የሚወጉ መንግሥታት የሚያገኛቸው መከራ ከዚህ ጋር ይመሳሰላል (ዘካ14፥13)::

2፥23 *በዚያን ቀን፤* የጌታ ቀን ማለት ነው (ኢሳ 2፥11:17: 20፤10፥20:27፤ ዘካ2፥11 እና ማብ ይመ):: *ባሪያዬ፤* ነቢያት (ኢሳ20፥3 እና ማብ ይመ)፣ አገር መሪዎች (ኢሳ22፥20) እንዲሁም መሲሑ ተጠርተውበታል (ኢሳ41፥8-9፤42፥1 እና ማብ ይመ):: *ማተሚያ ቀለበቴ፤* በዘመናችን አንድን ነገር ለማረጋገጥ ፊርማ እንደሚያስፈልገን ሁሉ፣ በዚያን ጊዜ እንደ ፊርማ የሚያገለግል ማኅተም ሲሆን (አስ8፥8 ይመ)፤ እንደ ቀለበት በጣት ላይ ይጠለቅ ነበር (አስ3፥10):: እንደ ሌሎቹ ማኅተሞች(ዘፍ38፥18ይመ) ሙሉ ዋጋ መከፈሉን ለማረጋገጥና ለሌሎችም ጕዳዮች ማስተማመኛ ሆኖ ያገለግል ነበር:: ቀለበቱ እዚህ ቦታ መጠቀሱ በንጉሥ ኢዮአቄም ላይ የደረሰበትን ርግማን (ኤር22፥24) የሚሻር ሳይሆን አይቀርም (ከመሳ17፥2 ጋር ያነጻጽሩ):: ከዳዊት ዘር መሲሑ አንድ ቀን እንደሚመጣ ዘሩባቤል ዋስትና ሆኖ ቀርቦአል (ከማቴ1፥1:12 ጋር ያነጻጽሩ):: በ2ቆሮ1፥22 ላይ መንፈስ ቅዱስ አማኝ ወደፊት ለሚወርሰው የእግዚአብሔር መንግሥት ርስት መያዣ መሆኑ ተጠቅሶአል (ከኤፌ1፥13-14 ጋር ያነጻጽሩ):: *መርጬሃለሁና፤* ኢሳ 41፥8-9፤42፥1እና ማብ ይመ::

# ትንቢተ ዘካርያስ

## መግቢያ

### ታሪካዊ ዳራው

ዘካርያስ የትንቢት አገልግሎት የሰጠው ከምርኮ ዘመን በኋላ ሲሆን፣ አይሁድ ከባቢሎን ምርኮ በተመለሱበት ጊዜ ነበር፤ ዝርዝር ታሪኩን በሚገባ ለመረዳት ከትንቢተ ሐጌ መግቢያ ላይ "ታሪካዊ ዳራው" የሚለውን ይመ::

### ጸሐፊውና የጽሑፉ ወጥነት

ኤርምያስ (1፥1) እና ሕዝቅኤል (1፥3) ነቢይ ብቻ ሳይሆኑ ካህንም እንደ ነበሩ ሁሉ፣ ዘካርያስም ነቢይና ካህን ነበር (1፥1):: ዘካርያስ የተወለደው በባቢሎን ሲሆን፣ በዘሩባቤልና በኢያሱ መሪነት በ538 ዓ.ቅ.ክ ወደ ይሁዳ ከተመለሱት ሰዎች መካከል አንዱ ነበር:: በነህ 12፥4 ላይ አያቱ አዶ ከምርኮ ከተመለሱት ሰዎች ዝርዝር ውስጥ ተጠቅሶአል:: በኋላም ኢዮአቄም ሊቀ ካህን በነበረበት ጊዜ፣ ዘካርያስ ከካህናት ወገን ለነበሩት አለቃ በመሆን (ነህ 12፥10-16) አዶን ተክቶአል (1፥1 :7)፤ ዘካርያስ የአያቱን ቦታ ሊይዝ የቻለው አባትየው (በራክዩ፣ 1፥1 :7) በወጣትነቱ ስለ ሞተ ነው የሚል ግምት አለ::

ዘካርያስ የነበረው ሐጌ በነበረበት ዘመን ነው (ዕዝ 5፥1፤ 6፥14)፤ ነገር ግን ከእርሱም በኋላ ለብዙ ጊዜ አገልግሎአል (1፥1 እና 7፥1 ከሐጌ 1፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ ነህ 12፥1-16 ማብ ይመ):: በወጣትነት ዕድሜው አገልግሎት በመጀመሩ (2፥4 ይመ)፣ እስከ ቀዳማዊ አርጤክስስ ዘመነ መንግሥት (465-424 ዓ.ቅ.ክ) ድረስ ቈይቶ ሊያገለግል ችሎአል::

በስሙ የተጠራውን ይህን መጽሐፍ ዘካርያስ ሙሉ በሙሉ ሳይጽፍ አይቀርም:: አንዳንድ ምሁራን ከም 1-8 ያለውን ክፍል የጻፈው ጸሐፊ ከም9-14 ያለውን ከጻፈው እንደሚለይ በማገለጽ የተጻፈበትን ስልትና የቅንብር ይዘቱን፣ እንዲሁም ታሪካዊ ሁነቶችንና የዘመን አቈጣጠር በማስረጃነት ያቀርባሉ:: ዘካርያስ የመጽሐፉ ጸሐፊ አለመሆኑን ለማገለጽ የቀረበው ይህ ተቃውሞ አጥጋቢ አይደለም፤ የመጽሐፉንም ወጥነት አጠራጣሪ ሊያደርግ አይችልም::

### የተጻፈበት ጊዜ

የዘካርያስ መልእክት የተጻፈበት ጊዜ ከሐጌና ከሌሎች ታሪካዊ ድርጊቶች ጋር የተያያዘ ነው:: ከዚህ በታች እንደተመለከተው፤

1) የመጀመሪያው የሐጌ መልእክት (ሐጌ 1፥1፤ ዕዝ 5፥1)፣ በ520 ዓ.ቅ.ክ
2) የቤተ መቅደሱ እንደ ገና መሠራት መጀመር (ሐጌ 1፥12-15፤ ዕዝ 5፥2)፣ በ520 ዓ.ቅ.ክ
   - የቤተ መቅደሱ ሥራ መስተጓጐል (ዕዝ 4፥1-5)፣ ከ536-530 ዓ.ቅ.ክ
   - የሥራው ፈጽሞ መቆም (ሐጌ 2፥1-9)፣ ከ530-520 ዓ.ቅ.ክ
3) ሁለተኛው የሐጌ መልእክት (ሐጌ 2፥1-9)፣ በ520 ዓ.ቅ.ክ
4) የዘካርያስ ስብከት መጀመሪያ (1፥1-6)፣ በ520 ዓ.ቅ.ክ
5) ሦስተኛው የሐጌ መልእክት (ሐጌ 2፥10-19)፣ በ520 ዓ.ቅ.ክ
6) አራተኛው የሐጌ መልእክት (ሐጌ 2፥20-23)፣ በ520 ዓ.ቅ.ክ
7) የቤተ መቅደሱ እንደ ገና መሠራት አስመልክቶ የተንተናይ ደብዳቤ ለዳርዮስ (ዕዝ 5፥3-6፥14) 519-ከ518 ዓ.ቅ.ክ

- ቤተ መቅደሱ እንደ ገና መሠራት በመጀመሩና በተንትናይ መምጣት መካከል የጊዜ ክፍተት አለ::

8) የዘካርያስ ስምንቱ ራእዮች (ም 1፥7-6፥8)፣ በ519 ዓ.ቅ.ክ
9) ኢያሱ አክሊል መድፋቱ (ም 6፥9-15)፣ በ519 ዓ.ቅ.ክ
10) የንስሓ ጥሪና የበረከት ተስፋ (ም 7-8)፣ በ518 ዓ.ቅ.ክ
11) የቤተ መቅደሱ መመረቅ (ዕዝ 6፥15-18)፣ በ516 ዓ.ቅ.ክ
12) የዘካርያስ የመጨረሻ ትንቢት (ም 9-14)፣ ከ480 ዓ.ቅ.ክ በኋላ

### የተጻፈበት ምክንያትና ዐላማው

ትንቢተ ዘካርያስ የተጻፈበት ምክንያት ከትንቢተ ሐጌ ጋር ይመሳሰላል (ከሐጌ ታሪካዊ ዳራ "የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ):: ዘካርያስና ሐጌ መንፈሳዊ ተሐድሶ እንዲመጣ የሚፈልጉ ቢሆንም የሁለቱም ነቢያት ዋና ዐላማ የይሁዳን ሕዝብ መገሠጽና የጀመሩትን የቤተ መቅደሱን ሥራ እንዲጨርሱ ማደፋፈር ነበር (4፥8-10 ፤ ሐጌ 1፥2)፤ እንዲሁም በ1፥7-6፥8 ላይ የተጠቀሱት የሳምንቱ የሌሊት ራእዮች ዐላማ ምን እንደ ሆነ፣ በ1፥3፡5-6 ላይ ተገልጦአል:: እግዚአብሔርም ይሁዳ ወደ እርሱ ብትመለስ ወደ እርሷ እንደሚመለስ ተናግሮአል፤ የተናገረውም ቃል ሁልጊዜ ይፈጸማል::

### ትምህርተ መለኮታዊ አስተምህሮው

የመጽሐፉ ትምህርተ መለኮታዊ አስተምህሮ፣ መሲሐዊ እንዲሁም አቡቀለምሲሳዊና ሥነ ፍጻሜያዊ ከሆነ ዐቢይ ሐሳቡ ጋር የተያያዘ ነው:: ዘካርያስ ስለ መሲሑ ሁኔታ በሚገልጽበት ጊዜ፣ ክርስቶስ

ትሑት ሆኖ እንደሚመጣ (6፥12)፣ ሰው መሆኑን (6፥12፤ 13፥7)፣ እንደሚናቅና በሠላሳ ብር እንደ ሚሸጥ (11፥12-13)፣ እንደሚሰቀል (13፥7)፣ ክህነቱን (6፥13)፣ ንጉሥነቱን (6፥13፤ 9፥9፤ 14፥9:16)፣ በክብር እንደሚመጣ (14፥4)፣ የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ እንደሚሠራ (6፥12-13)፣ የአገዛዙ ሁኔታ ምን እንደሚመስል (9፥10፤ 14)፣ ዘላቂ ሰላምንና ብልጽግናን (3፥10፤ 9፥9-10) እንደሚያመጣ አስ ቀድሞ ተናግሮአል። እነዚህ መሲሑን የሚያመለክቱ ምንባቦች ኢየሱስ በሉቃስ 24፥25-27:44 ላይ ለተ ናገረው ነገር የበለጠ ትርጉም ይሰጡታል።

አቡቀለምሲሳዊና ሥነ ጽሑፋዊ ይዘቱን በሚመለከት ያለውን ሁኔታ ሲገልጽ ኢየሩሳሌም እንደም ትከበብ (12፥1-3፤ 14፥1-2)፣ በመጀመሪያ የይሁዳ ጠላቶች ድል እንደሚያደርጉ (14፥2)፣ እግዚአብሔር ስለ ኢየሩሳሌም እንደሚዋጋ (14፥3-4)፣ በሕዝብ ላይ ፍርድ እንደሚሆን (12፥9፤ 14፥3)፣ የይሁዳ መሬት አቀማመጥ እንደሚለወጥ (14፥4-5)፣ በመሲሑ ዘመነ መንግሥት የዳስ በዓሏ እንደሚከበር (14፥16-19)፣ ኢየሩሳሌምና ሕዝቧ በመጨረሻ እንደሚቀደሱ (14፥20-21) ዘካርያስ ትንቢት ተናግሮአል።

“እግዚአብሔር ያስታውሳል” የሚል ትርጉም ያለው የነቢዩ ስምም ትምህርተ መለኮታዊ ይዘት አለው። “እግዚአብሔር” የሚለው የአምላክ የግልና የቃል ኪዳን ስሙ ነው፤ ይህም እግዚአብሔር ለሰጠው ተስፋ ታማኝነቱን የሚገልጽ ዘላለማዊ ምስክር ነው (የዘፀ 3፥14 ማብ ይመ)። እግዚአብሔር የኪዳኑን ተስፋ ያስታውሳል፤ ይፈጽመውም ዘንድ ይተጋል። በዘካርያስ መጽሐፍ ውስጥ እስራኤላውያን የባቢሎን ግዞተኞች ከመሆን ነጻ እንደሚወጡ፣ መንግሥታቸው እንደሚመሠረትና አገልግሎት የሚሰጥ ቤተ መቅደስ እንደሚኖራቸው፣ እግዚአብሔር የሰጠው ተስፋ፣ በመሲሑ የሚሆነው ድነትና መታነጽ ምን እንደሚመስል ተብራርቶአል።

በአጠቃላይ መጽሐፉ ቀድሞም ሆነ ዛሬ፣ ወደፊትም እግዚአብሔር በታሪክ ውስጥ በሕዝብና በመንግሥታት ላይ ሉዓላዊ እንደ ሆነ የሚያመለክት ነው።

## ሥነ ጽሑፋዊ ቅርጽና መሪ ሐሳብ

ይህ መጽሐፍ ለንስሓ የሚጋብዝ ልመናን (1፥2-6)፣ ትንቢታዊ ራእዮችን (1፥7-6፥8)፣ የፍርድና የድነት ንግሮችን አካቶ የያዘ ነው (ም 9-14)። በ1፥7-6፥8 ላይ የተጠቀሱት ትንቢታዊ ራእዮች አቡቀ ለምሲሳዊ ጽሑፎች ሲሆኑ፣ ለእግዚአብሔር ሕዝብ መጽናናትን የሚሰጡ ጽሑፎች ናቸው። አቡቀለምሲ ሳዊው ክፍል በም 9-14 ከተጠቀሰው የድነት ቃል ጋር አብሮ ሲነበብ፣ የመጽሐፉ ዋና ሐሳብ በማ ጽናናት ላይ ያተኮረ እንደ ሆነ መረዳት ይቻላል፤ ይህም የእግዚአብሔር ሕዝብ ወደ ፊት ታላቅ ክብር የሚጠብቀው በመሆኑ ነው።

በመሠረቱ መጽናናትና ማበረታታት የመጽሐፉ ዐቢይ ሐሳብ ነው፤ የመጀመሪያው ማበረታ ትትም እንደ ገና እየተሠራ ያለውን ቤተ መቅደስ በሚያጠናቅቁበት ሁኔታ ላይ ያተኮረ ነው። ይህንም ከግብ ለማድረስና ለማጠናቀቅ የተለያዩ ስልቶች ተግባር ላይ ውለዋል፤ ይህም የመሪ ሐሳቡ አካል ነበር፤ ለምሳሌ የእግዚአብሔር አገዛዝ በመጨረሻ ሙሉ በሙሉ በምድር ላይ ይሰፍን ዘንድ መሲሑ ሲመጣ ታላቅ ጭንቀት እንደሚሆንና መንግሥቱን የሚቃወሙትንም ሁሉ እንደሚያስወግድ በአፅንዖት ይገልጻል።

## አስተዋፅዖ

ክፍል 1 (ም 1-8)

1. መግቢያ (1፥1-6)
   - ሀ. የተጻፈበት ጊዜና የጸሓፊው ስም (1፥1)
   - ለ. የንስሓ ጥሪ (1፥2-6)
2. በሌሊት የታዩ ስምንት ተከታታይ ራእዮች (1፥7-6፥8)
   - ሀ. በፈረስ ተቀምጦ በባርሰነት ዛፎች መካከል የቆመው ሰው (1፥7-17)
   - ለ. አራት ቀንዶችና አራት ጠራቢዎች (1፥18-21)
   - ሐ. የመለኪያ ገመድ የያዘ ሰው (ም 2)
   - መ. ለሊቀ ካህኑ የተሰጠው ንጹህ ልብስ (ም 3)
   - ሠ. የወርቁ መቅረዝና ሁለቱ የወይራ ዛፎች (ም 4)
   - ረ. በራሪው የመጽሐፍ ጥቅልል (5፥1-4)
   - ሰ. በኢፍ መስፈሪያ ውስጥ የተቀመጠችው አንዲት ሴት (5፥5-11)
   - ሸ. አራቱ ሠረገሎች (6፥1-8)
3. በሊቀ ካህኑ በኢያሱ ላይ የተጫነው የመታሰቢያ አክሊል (6፥9-15)
4. ትክክለኛ ያልሆነ ጾም፣ ስለ ወደፊቱ የተሰጠ ተስፋ (ም 7-8)
   - ሀ. ከቤቴል ተወክለው የመጡ ሰዎች ያቀረቡት ጥያቄ (7፥1-3)
   - ለ. የጌታ ተግሣጽ (7፥4-7)
   - ሐ. ንስሓ እንዲገቡ የተሰጠ ትእዛዝ (7፥8-14)
   - መ. ከእግዚአብሔር ሞገስ የተነሣ የእስራኤል ተሐድሶ (8፥1-17)
   - ሠ. በመንግሥቱ ውስጥ የሚሆነው ደስታና የአይሁድ ሞገስ ማግኘት (8፥18-23)

ክፍል 2 (ም 9-14)

5. ሁለት ትንቢታዊ ንግሮች፦ የመሲሑ መምጣትና የእግዚአብሔር መንግሥት በሚገባ መታወቅ፤ (ም 9-14)
    ሀ. የመጀመሪያው ንግር፦ የመሲሑ መምጣትና ተቀባይነት ማጣት (ም 9-11)
        1. መሲሕ የሆነው ንጉሥ እንደሚመጣ (ም 9-10)
        2. እረኛውና ንጉሡ መሲሕ ተቀባይነት ማጣቱ (ም 11)
    ለ. ሁለተኛው ንግር፦ የመሲሑ መምጣትና ተቀባይነት ማግኘት (ም 12-14)
        1. የእስራኤል ነጻ መውጣትና መለወጥ (ም 12-13)
        2. የመሲሑ መምጣትና መንግሥቱ (ም 14)

## ሕዝቡ ወደ እግዚአብሔር እንዲመለስ የቀረበ ጥሪ

**1** ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት በስምንተኛው ወር የእግዚአብሔር ቃል ወደ አዶ ልጅ ወደ በራክዩ ልጅ ወደ ነቢዩ ዘካርያስ እንዲህ ሲል መጣ፤

[2]"እግዚአብሔር በአባቶቻችሁ ላይ እጅግ ተቈጥቶ ነበር፤ [3]ስለዚህ ለሕዝቡ ንገር፤ እግዚአብሔር ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ 'ወደ እኔ ተመለሱ' ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፤ 'እኔም ወደ እናንተ እመለሳለሁ፤' ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፤ [4]የቀደሙት ነቢያት፣ 'እግዚአብሔር ጸባኦት፣ "ከክፉ መንገዳችሁና ከክፉ ሥራችሁ ተመለሱ" ይላል፤ በማለት ለአባቶቻችሁ ሰብከው ነበር፤ እነርሱ ግን አልሰሙም፤ እኔንም አላደመጡም፤ እንደ እነርሱ አትሁኑ፤ ይላል እግዚአብሔር። [5]አባቶቻችሁ አሁን የት አሉ? ነቢያትስ ለዘላለም በሕይወት ይኖራሉን? [6]ለባሪያዎቼ ለነቢያት ያዘዝኋቸው ቃልና ሥርዐት በአባቶቻችሁ ላይ አልደረሰምን?

"እነርሱም ንስሓ ገብተው፤ እንዲህ አሉ፤ 'እግዚአብሔር ጸባኦት በወሰነው መሠረት፣ ለሥራችንና ለመንገዳችን የሚገባውን አድርጎብናል።' "

## በባርሰነት ዛፎች መካከል የቆመው ሰው

[7]ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት፣ ሳባጥ በሚባለው በዐሥራ አንደኛው ወር በሃያ አራተኛው ቀን፣ የእግዚአብሔር ቃል ወደ አዶ ልጅ ወደ በራክዩ ልጅ ወደ ነቢዩ ዘካርያስ እንዲህ ሲል መጣ፤

[8]በምሽት ራእይ አየሁ፤ እዚያም በፊቴ አንድ ሰው በመጋላ ፈረስ ላይ ተቀምጦ አለ፤ እርሱም በሸለቆ ውስጥ በባርሰነት ዛፎች መካከልም ቆሞ ነበር፤ ከበስተ ኋላውም መጋላ፣ ሐመርና አንባላይ ፈረሶች ነበሩ።

[9]እኔም፣ "ጌታዬ ሆይ፤ እነዚህ ምንድን ናቸው?" አልሁ።

ከእኔ ጋር ይነጋገር የነበረው መልአክም፣ "እነዚህ ምን እንደ ሆኑ አሳይሃለሁ" አለኝ።

[10]ከዚያም በባርሰነት ዛፎች መካከል የቆመው ሰው፣ "እነዚህ በምድር ሁሉ እንዲመላለሱ እግዚአብሔር የላካቸው ናቸው" ሲል መለሰ። [11]እነርሱም በባርሰነት ዛፎች መካከል ቆሞ ለነበረው የእግዚአብሔር መልአክ፣ "በምድር ሁሉ ተመላለስን፤ መላዋ ምድርም ዐርፋ በሰላም ተቀምጣለች" ብለው መለሱለት።

[12]ከዚያም የእግዚአብሔር መልአክ፣ "እግዚአብሔር ጸባኦት ሆይ፤ በእነዚህ ሰባ ዓመታት ውስጥ የተቈጣሃቸውን ኢየሩሳሌምንና የይሁዳን ከተሞች የማትምራቸው እስከ መቼ ነው?" አለ። [13]እግዚአብሔርም ከእኔ ጋር ይነጋገር ለነበረው መልአክ ደስ በሚያሰኝና በሚያጽናና ቃል መለሰለት።

[14]ከዚያም ከእኔ ጋር ይነጋገር የነበረው መልአክ እንዲህ አለኝ፤ "ይህን ቃል ተናገር፤ እግዚአብሔር ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ 'ስለ ጽዮንና ስለ ኢየሩሳሌም እጅግ ቀንቻ

1፥1 ቍ7፤ዕዝ 4፥24፤ 5፥1፤6፥15፤ ነህ12፥4፤ማቴ23፥35፤ ሉቃ11፥51
1፥2 2ዜና36፥16
1፥3 ኢዮ22፥23፤ ሚል3፥7፤ያዕ4፥8
1፥4 2ነገ17፥13፤ 2ዜና፤24፥19፤36፥ 15፤መዝ78፥8፤106፥ 6፤ኤር6፥17፥23፤ 23፥22፤ሕዝ20፥18፤ 33፥4፤ዘካ7፥7
1፥6 ዘዳ28፥2፤ ኢሳ44፥26፤ ኤር12፥14-17፤ 23፥20፤39፥16፤ 44፥17፤ሰቆ2፥17፤ ዳን9፥12፤ሆሴ5፥9
1፥7 ቍ1
1፥8 ዘካ6፥2-7፤ ራእ6፥4
1፥9 ዳን7፥16፤ ዘካ4፥14-5፤5፥5
1፥10 ዘካ6፥5-8
1፥11 ዘፍ16፥7፤ ኢሳ14፥7
1፥12 2ዜና36፥21፤ መዝ6፥3፤40፥11፤ ኤር40፥5፤ዳን9፥2
1፥13 ኢዮ15፥11፤ ኢሳ35፥4፤ዘካ4፥1
1፥14 ኢሳ26፥11፤ ኢል2፥18

1፥1፤ *በሁለተኛው ዓመት በስምንተኛው ወር፤* በ520 ዓ.ቅ.ክ ከጥቅምት እስከ ኅዳር ያለውን ጊዜ የሚያመለክት ነው። ሐጌም፣ ዳርዮስ በነገሠ በሁለተኛው ዓመት ፣በስድስተኛው ወር፣ በመጀመሪያው ቀን ማለትም ነሐሴ 29 ቀን 520 ዓ.ቅ.ክ (ሐጌ 1፥1) የነቢይነት አገልግሎቱን ጀመረ። *የእግዚአብሔር ቃል፤* የትንቢትን ቃል መገለጥ የሚያመለክት የተለመደ ሐረግ ነው(9፥1፤12፥1፤ ኤር1፥2፤ ሕዝ1፥3፤ሆሴ1፥1፤ኢዩ1፥1፤ ዮና1፥1፤3፥1፤ሚክ1፥1፤ሶፎ1፥1፤ ሐጌ1፥1፤ሚል1፥1ይመ፤እንዲሁም የ6፥9ማብ ይመ። *አዶ፤* ቍ7፤ ዕዝ 5፥1፤6፥14፤ነህ12፥4:16 ይመ። እንዲሁም ከመግቢያው "ጸሐፊው" የሚለውን ይመ። *ነቢዩ፤* የእግዚአብሔር አፍ ለመሆን በራሱ በእግዚአብሔር የተጠራ ማለት ነው የዘፀ7፥1-2 ማብ ይመ።

1፥2፤ *በአባቶቻችሁ ላይ እጅግ ተቈጥቶ ነበር፤* ከባቢሎን ምርኮ በፊት የነበሩት የአይሁድ አባቶች፣ ኪዳኑን በማፍረስ እግዚአብሔርን ስለ በደሉ እግዚአብሔር ቀጣቸው፤ ከዚህም የተነሣ በ586 ዓ.ቅ.ክ ላይ ኢየሩሳሌም ተደመሰሰች፤ ሕዝቡም ወደ ባቢሎን ተጋዘ። እግዚአብሔር የሚቀጣ መሆኑን መካድ ሁለንተናዊ ማንነት ያለው አምላክ መሆኑን መካድ ነው።

1፥3፤ *'ወደ እኔ ተመለሱ'... 'እኔም ወደ እናንተ እመለሳለሁ'፤* ከ7፥13 ጋር ያነጻጽሩ። በዘካርያስ ዘመን የነበሩ ሰዎች አባቶቻቸው የሄዱበትን ክፉ መንገድ በመተው (ቍ4) ወደ እግዚአብሔር ቢመለሱ፣ እግዚአብሔር ወደ እነርሱ ይመለሳል፤ በርግጥም ፈንታ በረከትን ያፈስስላቸዋል ቍ16፤ ኤር18፥710 ይመ።

1፥4፤ *የቀደሙት ነቢያት፤* እንደ ኢሳይያስ (ኢሳ 45፥22 ይመ)፣ እንደ ኤርምያስና (ኤር18፥11 ይመ) ሕዝቅኤል (ሕዝ 33፥11 ይመ) ያሉትን ነው። እንዲሁም 7፥7:12፤ ኤር25፥4-5፤ 35፥15 ይመ።

1፥5፤ *ለዘላለም በሕይወት ይኖራሉን?* አይኖሩም፤ በእነርሱ የተነገረው የእግዚአብሔር ቃል ግን እስኪፈጸም ድረስ ይኖራል (ቍ6 ይመ)።

1፥6፤ *ያዘዝኋቸው ቃልና...በአባቶቻችሁ ላይ አልደረሰምን?* ከኢሳ 40፥6-8፤55፥10-11ጋር ያነጻጽሩ። "አልደረሰምን?" የሚለውን ዘይቤያዊ አገላለጽ በተመለከተ በዘዳ28፥2:15:45 ይመ። *ለባሪያዎቼ ለነቢያት፤* 2ነገ9፥7፤17፥13:23፤21፥10፤24፥2፤ ዕዝ9፥11፤ኤር7፥25 እና ማብ ይመ፤25፥4፤ ሕዝ38፥17፤ዳን 9፥6:10፤ አሞ3፥7ይመ። *ንስሓ ገብተው፤* ከምርኮ በፊት በነበሩት አባቶች ላይ፣ በምርኮ ወቅት ደግሞ በልጆቻቸው ላይና ከምርኮ በኋላም በነበሩት ላይ የደረሰውን ማመልከቱ ግልጽ ነው ከዕዝ 9፤10፥1-17፤ከዳን 9፥1-19ጋር ያነጻጽሩ።

1፥7-17፤ የዘካርያስ የመጀመሪያው ራእይ ነው። የእግዚአብሔር የኪዳን ሕዝብ በመከራ ውስጥ ሳሉ ጠላቶቻቸው ቢመቻቸውም፣ እግዚአብሔር ለሕዝቡ የሚቀና በመሆኑ (የዘፀ 20፥5 ማብ ይመ) ሕዝቡን፣ ከተማቸውንና ቤተመቅደሱን መልሶ ያድሳል። በዚህ በመጀመሪያ ራእይ ውስጥ ያሉት ምሳሌያዊ ገለጻዎች በስምንተኛውና በመጨረሻው ራእይ ውስጥም ተንጸባርቀዋል 6፥1-8።

1፥7፤ *ሳባጥ...በሃያ አራተኛው ቀን፤* የካቲት 15 ቀን 519 ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው። ይህም በቍ1 ላይ ከተጠቀሰው ቀን ሦስት ወር በላይ ነው።

1፥8፤ *በምሽት፤* ዘካርያስ ስምንቱንም ራእዮች ያየው በአንዲት ምሽት ነበር 1፥7-6፥8። *ራእይ፤* ሕልም አይደለም 4፥1ይመ። ለዘካርያስ ራእይ የተሰጠው ከእንቅልፉ ሙሉ ለሙሉ ነቅቶ ሳለ ነው። *አንድ ሰው...ላይ ተቀምጦአል፤* የእግዚአብሔር መልአክ ነው ቍ11። በቍ9፥13-14:19፤2፥3፤4፥1:4-5፤5፥5:10፤ 6፥4-5 ላይ ከተጠቀሰውና ራእዩን ከሚተረጕመው መልአክ ይለያል። *ፈረሶች፤* የተላኩ መላእክት ሊሆኑ ይችላሉ ቍ10።

1፥11፤ *የእግዚአብሔር መልአክ፤* የዘፍ16፥7 ማብ ይመ። *ዐርፋ፤* ከ6፥8 ጋር ያነጻጽሩ። የፋርስ መንግሥት በሰላም የሚኖርበት ጊዜ ቢሆንም ቍ15፣ በይሁዳ ያሉት አይሁድ ግን በባዕድ መንግሥት ተጽእኖ ሥር ነበሩ ቍ12።

1፥12፤ *ሰባ ዓመታት፤* 7፥5እና ማብ ይመ። ኤር25፥11-12 እና ማብ ይመ፤ 29፥10 ይመ፤ ከ2ዜና36፥21፤ዕዝ1፥1፤ዳን9፥2 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥13፤ *በሚያጽናና ቃል፤* ከቍ14-17 ያሉትን ያመለክታል።

1፥14፤ *ቀንቻለሁ፤* 8፥2 ይመ። እግዚአብሔር ለይሁዳ ያለውን ፍቅር የሚያሳይ ነው። የዘፀ20፥5 ማብ ይመ፤ ከያዕ4፥4 ጋር ያነጻጽሩ። ዋና ሐሳቡም በይሁዳ ላይ የተፈጸመውን ዐመፅ እግዚአብሔር ይበቀላል የሚል ነው (ቍ15)።

ለሁ፤ 15ሰላም አለ በሚሉ አሕዛብ ላይ ግን በጣም ተቈጥቻለሁ፤ በመጠኑ ተቈጥቼ ሳለሁ፣ እነርሱ ግን ጥፋቱ እንዲብስ አደረጉ።'

16"ስለዚህ *እግዚአብሔር* እንዲህ ይላል፤ 'በምሕረት ወደ ኢየሩሳሌም እመለሳለሁ፤ በዚያም ቤቴ እንደ ገና ይሠራል፤ መለኪያ ገመድም በኢየሩሳሌም ላይ ይዘረጋል' ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት።

17"ቀጥለህም እንዲህ እያልህ ስበክ፤ *እግዚአብሔር* ጸባኦት እንዲህ ይላል፤ 'ከተሞቼ እንደ ገና ብልጽግና ይትረፈረፍባቸዋል፤*እግዚአብሔርም* እንደ ገና ጽዮንን ያጽናናል፤ ኢየሩሳሌምንም ይመርጣል።'"

## አራቱ ቀንዶችና አራቱ የእጅ ሙያተኞች

18ከዚያም ወደ ላይ ተመለከትሁ፤ ከፊቴም አራት ቀንዶችን አየሁ፤ 19ከእኔ ጋር ይነጋገር የነበረውንም መልአክ፣ "እነዚህ ምንድን ናቸው?" አልሁት።

እርሱም፣ "እነዚህ ይሁዳን፣ እስራኤልንና ኢየሩሳሌምን የበታተኑ ቀንዶች ናቸው" አለኝ።

20ከዚያም *እግዚአብሔር* አራት የእጅ ሙያተኞችን አሳየኝ። 21እኔም፣ "እነዚህስ ምን ሊያደርጉ መጡ?" አልሁ።

እርሱም፣ "እነዚህ ቀንዶች ማንም ራሱን ቀና ማድረግ እንዳይችል ይሁዳን የበታተኑ ናቸው፤ እነዚህ የእጅ ሙያተኞች ግን የመጡት እነርሱን ሊያስደነግጧቸው፣ ሕዝቡን ለመበታተን በይሁዳ ምድር ላይ ቀንዳቸውን ያነሡትን የእነዚህን የአሕዛብ ቀንዶች ሰብሮ ለመጣል ነው" አለኝ።

## የመለኪያ ገመድ የያዘ ሰው

**2** ደግሞም ወደ ላይ ተመለከትሁ፤ እነሆ፤ በእጁ የመለኪያ ገመድ የያዘ ሰውም በፊቴ አየሁ፤ 2እኔም፣ "የት ልትሄድ ነው?" አልሁት።

እርሱም፣ "የኢየሩሳሌም ርዝመትና ስፋት ምን ያህል እንደ ሆነ ለመለካት መሄዴ ነው" አለኝ።

3ከእኔ ጋር ይነጋገር የነበረው መልአክም ሄደ፤ ሌላም መልአክ ሊገናኘው መጣ፤ 4እንዲህም አለው፣ "ሩጥና ለዚያ ጕልማሳ እንዲህ ብለህ ንገረው፤ 'በውስጧ ካለው የሰውና የከብት ብዛት የተነሣ፣ ኢየሩሳሌም ቅጥር እንደሌላት ከተማ ትሆናለች፤ 5እኔ ራሴ በዙሪያዋ የእሳት ቅጥር እሆንላታለሁ' ይላል *እግዚአብሔር* 'በውስጧም ክብሯ እሆናለሁ።'

6"ኑ! ኑ! ውጡ ከሰሜን ምድር አምልጡ" ይላል *እግዚአብሔር*፤ "ለአራቱ የሰማይ ነፋሳት በትኛችኋለሁና፤" ይላል *እግዚአብሔር*።

7"አንቺ ጽዮን ነዪ፤ ከባቢሎን ሴት ልጅ ጋር የምትኖሪ ሆይ፤ ኰብልዪ።" 8*እግዚአብሔር* ጸባኦት እንዲህ ይላልና፤ "ካከበረኝና በዘረፉአችሁ አሕዛብ ላይ ከላከኝ በኋላ፣ የሚነካችሁ የዐይኑን ብሌን ይነካል፤ 9እነሆ፤ እጄን በእነርሱ ላይ አነሣለሁ፤ ባሪያዎቻቸውም ይዘርፏቸዋል፤ ከዚያም *እግዚአብሔር* ጸባኦት እኔን እንደ ላከኝ ታውቃላችሁ።

10"የጽዮን ልጅ ሆይ፤ እልል በዪ፤ ደስም ይበልሽ፤ እኔ እመጣለሁና፤ በመካከልሽም እኖራለሁ" ይላል እግዚአብሔር። 11"በዚያ ቀን ብዙ አሕዛብ ወደ *እግዚአብሔር* ይጠጋሉ፤ የእኔም ሕዝብ ይሆናሉ። በመካከልሽ እኖራለሁ፤ *እግዚአብሔር* ጸባኦት ወደ አንቺ እንደላከኝም ታውቃላችሁ። 12*እግዚአብሔርም* በተቀደሰችው ምድር ይሁዳን ርስቱ አድርጎ ይወርሳል፤ ኢየሩሳሌምንም እንደ ገና ይመርጣል።

1፥15 2ዜና28፥9፤ መዝ51፥18፤ ኢሳ 14፥1፤ 40፥1፤54፥8-10፤61፥4
1፥16 ዕዝ1፥1፤ ኢዮ38፥5፤ ዘካ2፥1-2፤8፥3
1፥17 ዕዝ9፥9፤ መዝ51፥18፤ኢሳ 14፥1፤40፥1፤54፥8-10፤61፥4
1፥19 አሞ6፥13
1፥21 1ነገ22፥11፤ መዝ75፥4፡10፤ኢሳ 54፥16-17፤ ዘካ12፥9
2፥2 ሕዝ40፥3፤ ዘካ1፥16፤ራእ21፥15
2፥4 ኢሳ49፥20፤ ኤር30፥19፤33፥22፤ ሕዝ38፥11፤ዘካ14፥11
2፥5 መዝ46፥5፤ 85፥9፤125፥2፤ ኢሳ10፥17፤11፥10፤ 24፥23፤26፥1፤ ሕዝ 38፥14፤ 42፥20፤ ራእ21፥23
2፥6 መዝ44፥11፤ ሕዝ17፥21፤37፥9፤ ማቴ24፥31፤ማር 13፥27
2፥7 ኢሳ42፥7፤ 48፥20፤ኤር3፥18
2፥8 ዘዳ32፥10
2፥9 ኢሳ14፥2፤ 48፥16፤ኤር12፥14፤ ዕን2፥8፤ዘካ4፥9፤ 6፥15
2፥10 ዘፀ25፥8፤ ዘሌ26፥12፤ዘኍ 23፥21፤ኢሳ23፥12፤ ሶፎ3፥14፤ዘካ8፥3፤ 9፥9፤ራእ21፥3
2፥11 ኤር24፥7፤ ሚክ4፥2፤ዘካ4፥9፤6፥ 15፤8፥8፡20-22
2፥12 ዘፀ34፥9፤ ዘዳ12፥5፤መዝ 33፥12፤ኢሳ14፥1፤ ኤር10፥16፤40፥5

1፥15፤ *ጥፋቱ እንዲብስ አደረጉ፤* እግዚአብሔር በእስራኤል ላይ ስለተቈጣ፣ አሦራውያንንና (ኢሳ10፥5) ባቢሎናውያንን (ኢሳ47፥6፤ኤር25፥9) ተጠቅሞ ቢቀጣቸውም፣ አሦራውያንና ባቢሎናውያን ግን ከዚህ አልፎ በመሄድ የአይሁድን ሕዝብ ከምድረ ገጽ ለማጥፋት ሞከሩ።

1፥16፤ *በምሕረት፤* ወይም፣ "እናት ለልጅዋ ያላት ርኅራኄ" ዐይነት ነው ቍ12 ይመ። *እመለሳለሁ፤* የቍ3 ማብ ይመ። *ቤቴ እንደገና ይሠራል፤* ዕዝ6፥14-16 ይመ። *መለኪያ ገመድም፣* የተሐድሶ ምልክት ነው ከኤር31፥38-40 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥17፤ *ኢየሩሳሌምንም ይመርጣል፤* 2፥12፤3፥2 ይመ።

1፥18-21፤ የዘካርያስ ሁለተኛው ራእይ ነው፤ እስራኤልን ባድማ ያደረጉ መንግሥታት (ቍ19) እነርሱም እንደዚሁ በሌሎች መንግሥታት ፈጽመው ይጠፋሉ።

1፥18፤ *አራት፤* ቍጥሩ ቃል በቃል የሚወሰድ ከሆነ አሦርን፣ ግብፅን፣ ባቢሎንንና ሜዶንና ፋርስን የሚያመለክት ነው። *ቀንዶችን፤* በጥቅሉ የጥንካሬ ምልክት (መዝ18፥2) ወይም የአንድን አገር ብርታት ማለትም ንጉሥዋን (መዝ 89፥17፤ ዳን 7፥78፤ 8፥20-21፤ራእ17፥12) ወይም ቍ21 በዚህ ቦታ እንደተገለጸው በአጠቃላይ የአንድን ሕዝብ ኀይል የሚያመለክት ነው።

1፥20፤ *አራት የእጅ ሙያተኞችን፤* ቍጥሩ ቃል በቃል የሚወሰድ ከሆነ ግብፅን፣ ባቢሎን፣ፋርስንና ግሪክን የሚያመለክት ነው፤ ይህ የይሁዳ ጠላቶች በሙሉ በመጨረሻ እንደሚሸነፉ ግልጽ የሚያደርግ ነው (ቍ21)።

2፥1-13፤ የዘካርያስ ሦስተኛ ራእይ ነው። የቃል ኪዳኑ ሕዝብ፣ ቤተ መቅደሱና ከተማዋ ሙሉ በሙሉ እንደሚታደሱና እንደሚባረኩ የሚያመለክት ነው።

2፥1፤ *የመለኪያ ገመድ፤* የ1፥16 ማብ ይመ።

2፥4፤ *ጕልማሳ፤* ዘካርያስ መሆኑ ግልጽ ነው። *ቅጥር እንደሌላት፤* በቅጥር እስከማይወሰኑ ድረስ የከተማዋ ሕዝብ እጅግ ይበዛል 10፥8፡10፤ኢሳ49፥19-20 ማብ ይመ።

2፥5፤ *የእሳት ቅጥር፤* ለመለኮታዊው ጥበቃ ትእምርት ነው ዘፀ13፥21እና ማብ ይመ፤ኢሳ4፥56 እና ማብ ይመ። *ክብሯ፤* ዘፀ 40፥34 ይመ።

2፥6፤ *ከሰሜን ምድር፤* ባቢሎን (ቍ7) ከሰሜን መጥታ ነው ይሁዳን የወረረችው (ኤር1፥14፤4፥6፤6፥1፡22፤10፥22)። *ለአራቱ የሰማይ ነፋሳት፤* በሁሉም አቅጣጫ ማለት ነው። በምርኮ ያለው ሕዝብ ከሰሜን፣ ከደቡብ፣ ከምሥራቅና ከምዕራብ ተመልሶ ይመጣል ኢሳ43፥56፤49፥12።

2፥7፤ *ጽዮን፤* በባቢሎን ያሉ ከኢየሩሳሌም የተወሰዱ ምርኮኞችን ያመለክታል። *ከባቢሎን...ኰብልዪ፤* ከራእ18፥48 ጋር ያነጻጽሩ።

2፥8፤ *የዐይኑን ብሌን፤* የዘዳ32፥10 ማብ ይመ።

2፥9፤ *እጄን፤* የኀይል ምሳሌ ነው።

2፥10፤ 9፥9 ይመ። *በመካከልሽም እኖራለሁ፤* ቍ11፤8፥3፤ ዘሌ26፥11-12፤ሕዝ37፥27፤ ዮሐ1፥14፤2ቆሮ6፥16፤ራእ21፥3 ይመ።

2፥11፤ *ብዙ አሕዛብ፤* ለአብርሃም የተሰጠው ተስፋ ይፈጸም ዘንድ (ዘፍ12፥3ይመ፤ዘካ8፥20-23፤ዘፍ18፥18፤22፥18፤ኢሳ2፥2-4፤60፥3ጋር ያነጻጽሩ)። *በዚያ ቀን፤* የጌታን ቀን ያመለክታል (3፥10 እንዲሁም የኢሳ2፥11፡17፡20ማብ ይመ)።

2፥12፤ *በተቀደሰችው ምድር፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ምድሪቱ በዚህ መልኩ የተጠራችው በዚህ ስፍራ ብቻ ነው፤ ይህ የሆነበት ዋናው ምክንያት የቅዱሱ ንጉሥ የእግዚአብሔር ቤተ

[13]*እግዚአብሔር* ከተቀደሰ ማደሪያው ተንሥቶአልና፣ *ሥጋ* ለባሽ ሁሉ ሆይ፤ በፊቱ ጸጥ በል።

## ለሊቀ ካህኑ የሚሆን ንጹሕ ልብስ

**3** እርሱም ሊቀ ካህኑን ኢያሱን[a] *በእግዚአብሔር* መልአክ ፊት ቆሞ፣ ሰይጣንም[b] ሊከሰው በስተ ቀኙ ቆሞ አሳየኝ። [2]*እግዚአብሔርም* ሰይጣንን፣ "አንተ ሰይጣን፤ *እግዚአብሔር* ይገሥጽህ፤ ኢየሩሳሌምን የመረጠ *እግዚአብሔር* ይገሥጽህ፤ ይህ ሰው ከእሳት የተነጠቀ ትንታግ አይደለምን?" አለው።

[3]ኢያሱም ያደፈ ልብስ ለብሶ በመልአኩ ፊት ቆሞ ነበር። [4]መልአኩም ከፊቱ ቆመው የነበሩትን፣ "ያደፉ ልብሶቹን አውልቁለት" አላቸው።

ኢያሱንም፣ "እነሆ፤ ኀጢአትህን ከአንተ አስወግጃለሁ፤ ጥሩ ልብስም አለብስሃለሁ" አለው።

[5]እኔም፣ "ንጹሕ ጥምጥም በራሱ ላይ አድርጉለት" አልሁ። *የእግዚአብሔርም* መልአክ በአጠገቡ ቆሞ እያለ፣ ንጹሕ ጥምጥም በራሱ ላይ አደረጉለት፤ ልብስም አለበሱት።

[6]*የእግዚአብሔርም* መልአክ ለኢያሱ ይህን ማስጠንቀቂያ ሰጠው፤ [7]"*እግዚአብሔር* ጸባአት እንዲህ ይላል፤ 'በመንገዴ ብትሄድ፣ ትእዛዜንም ብትጠብቅ፣ ቤቴን ታስተዳድራለህ፤ በአደባባዮቼም ላይ ኀላፊ ትሆናለህ፤ በዚህ በቆሙት መካከል ቦታ እሰጥሃለሁ።

[8]" 'ሊቀ ካህኑ ኢያሱ ሆይ፤ ስማ፤ በፊትህ የሚቀመጡትም ረዳቶችህ ገና ወደ ፊት ለሚመጡት ምልክት የሚሆኑ ሰዎች ናቸውና ይስሙ፤ እነሆ፤ ባሪያዬን ቍጥቋጡን አመጣለሁ። [9]በኢያሱ ፊት ያስቀመጥሁት ድንጋይ እነሆ! በዚያ በአንዱ ድንጋይ ላይ ሰባት ዐይኖች[c] አሉ፤ በእርሱም ላይ ቅርጽ እቀርጻለሁ፤ የዚህችንም ምድር በደል በአንድ ቀን አስወግዳለሁ፤' ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት።

[10]" 'በዚያን ቀን እያንዳንዱ በግዛ ወይኑና በለሱ *ሥር* ሆኖ ባልንጀራውን ይጋብዛል፤' ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት።"

## የወርቁ መቅረዝና ሁለቱ የወይራ ዛፎች

**4** ከእኔ ጋር ይነጋገር የነበረው መልአክም ተመልሶ፣ አንድ ሰው ከእንቅልፉ እንደሚነቃ አነቃኝ፤ [2]እርሱም፣ "*ምን ታያለህ?*" አለኝ።

እኔም እንዲህ አልሁ፤ "እነሆ፤ በዐናቱ ላይ የዘይት ማሰሮ ያለበት ሁለንተናው ወርቅ የሆነ መቅረዝ አየሁ፤ በመቅረዙም ላይ ሰባት ቧንቧዎች ያሏቸው ሰባት መብ

2፥13 ዘፀ14፥14፤ ዘዳ26፥15፤ኢሳ41፥1
3፥1 2ሳሙ24፥1፤ 2ዜና18፥21፤ዕዝ2፥2፤ መዝ109፥6፤ዘካ6፥11፤ ማቴ4፥10
3፥2 ኢሳ7፥4፤ 14፥1፤ይሁ1፥9፡23
3፥4 ዘፍ41፥42፤ 2ሳሙ12፥13፤ መዝ132፥9፤ ኢሳ52፥1፤ሕዝ 36፥25፤ሚክ7፥18፤ ራእ19፥8
3፥5 ዘፀ29፥6
3፥7 ዘሌ8፥35፤ ዘዳ17፥8-11፤ 2ዜና23፥6፤ኤር15፥1 9፤ሕዝ44፥15-16፤ዘካ6፥15
3፥8 ዘዳ28፥46፤ ኢሳ4፥2፤49፥3፤ ሕዝ12፥11፤17፥22፤ ሐጌ1፥1
3፥9 2ሳሙ12፥13፤ 2ዜና16፥9፤ዕዝ2፥2፤ ኢሳ28፥16፤ ኤር50፥20
3፥10 ዘኁ 16፥14፤ 1ነገ4፥25፤ ኢዮ11፥18፤ሚክ4፥4
4፥1 ኤር31፥26፤ ዳን8፥18
4፥2 ዘፀ25፥31፤ ኤር1፥13፤ራእ 1፥12፤ 4፥5

[a]1 *የሆሹዋ* ለሚለው ተለዋጭ ስም ነው፤ እዚህ ላይ እንዲሁም በዘካርያስ መጽሐፍ በሌሎች ቦታ።
[b]1 *ሰይጣንም* ትርጕሙ ከሳሽ ማለት ነው።

መቅደስና ዙፋኑ በምድር የተቀመጠበት፣ እርሱም ከኪዳኑ ሕዝብ ጋር አብሮ የሚኖርበት ቦታ በመሆኑ ነው። የዘፀ3፥5 ማብ ይመ። *ኢየሩሳሌምንም..ይመርጣል፤* 1፥17፤3፥2 ይመ።

2፥13፤ *በፊቱ ጸጥ በል፤* ዕን 2፥20፤ ሶፎ1፥7ይመ። *ተንሥቶአልና፤* ሊፈርድ ማለት ነው ከቍ9 ጋር ያነጻጽሩ።

3፥1-10፤ የዘካርያስ አራተኛው ራእይ ነው፤ እስራኤል የካህናት ሕዝብ እንድትሆን ከኀጢአቷ ትነጻለች፤ እንደገናም ትታደሳለች (ዘፀ19፥6 እና ማብ ይመ)።

3፥1፤ *ኢያሱን፤* ይህ ሰው በዚህ ክፍል ኀጢአተኛ የሆነውን የእስራኤልን ሕዝብ ወክሎአል (ቍ8-9 ይመ)። በጥንት ጊዜ ይህ ስም የተለመደ ነበር፤ ግሪኩ ወደ አማርኛ ሲመለስ "ኢየሱስ" ማለት ሲሆን፣ "እግዚአብሔር ያድናል" ማለት ነው (የማቴ1፥21 ማብ ይመ)። *በእግዚአብሔር መልአክ፤* 1፥11ይመ፤ እንዲሁም የዘፍ16፥7 ማብ ይመ። *በ...ፊት ቆሞ፤* እንደ ካህን ሆኖ በፊቱ ማገልገሉን ያመለክታል (ዘዳ10፥8፤2ዜና29፥11፤ሕዝ44፥15 ይመ)። *ሰይጣንም፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። ከኢዮ1፥6፤2፤2፥1-7፤ራእ 12፥10 ጋር ያነጻጽሩ። *ሊከሰው፤* በዕብራይስጡ ይህ ቃልና ሰይጣን የሚለው ስም የተገኙት ከአንድ ቃል ነው። *በስተቀኙ፤* መዝ109፥6 ይመ።

3፥2፤ *ይገሥጽህ ይገሥጽህ፤* የተደገመው ለአጽንዖት ነው (4፥7 ይመ፤ እንዲሁም የኢሳ 40፥1 ማብ ይመ)። *ኢየሩሳሌምን የመረጠ፤* 1፥17፤2፥12 ይመ። *ከእሳት የተነጠቀ ትንታግ፤* አይሁድ ከባቢሎናውያን የምርኮ እሳት የዳኑት እግዚአብሔር ለእነርሱ ያለውን የወደፊት ዐላማና ዕቅድ እንዲፈጸ ነው፤ (አሞ4፥11፤ ዘካ13፥8-9፤ ዘዳ4፥20እና ማብ ይመ፤7፥7-8፤1ነገ8፥51፤ኢሳ48፥10፤ኤር 11፥4፤ 30፥7፤ራእ12፥13-16 ይመ)።

3፥4፤ *ከፊቱ ቆመው የነበሩትን፤* መላእክት ሳይሆኑ አይቀርም (እንዲሁም ቍ7ይመ)። *ያደፉ ልብሶቹን አውልቁለት፤* ለክህነት አገልግሎቱ የማያበቁትን ነው፤ ይህም ከኀጢአት የመንጻት ትእምርት ነው (የቍ9 ማብ ይመ)።

3፥5፤ *ንጹሕ ጥምጥም በራሱ ላይ አድርጉለት፤* ታላቅ ወደ ሆነ የክህነት አገልግሎት የተመለሰ በእግዚአብሔር ፊት ስለ እስራኤል እንዲቆም የተሾመ ካህን እስራኤል ማግኘቷን ያመለክታል። በጥምጥሙ ፊት፣ "ቅድስና ለእግዚአብሔር" የሚል ጽሑፍ ነበረበት (ዘፀ28፥36፤ 39፥30 ይመ፤ ከ14፥20ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥7፤ ኢያሱና ከእርሱ ጋር ያሉት ካህናት ታማኝ ከሆኑ እግዚአብሔር ለጽዮንና ለእስራኤል ያለውን ዐላማና ዕቅድ ከሚፈጽሙት መላእክት ጋር አብረው ይሠሩ ነበር። *በዚህ በቆሙት መካከል፤* የቍ4ማብ ይመ።

3፥8፤ *ረዳቶችህ፤* ከእርሱ ጋር የሚያገለግሉ ካህናት ናቸው። *ባሪያዬን፤* የዘፀ14፥31፤መዝ18ርእስ፤ኢሳ41፥8-9፤42፥1-4፤42፥1፤ ሮሜ 1፥1ማብ ይመ። *ቍጥቋጡን፤* ለመሲሑ የተሰጠ ስያሜ ነው (6፥12 ይመ፤ ኢሳ4፥2 እና ማብ ይመ፤11፥1፤ ኤር 23፥5፤ 33፥15 ይመ)።

3፥9፤ *ድንጋይ፤* ምናልባት ለመሲሑ የተሰጠ ሌላ ስያሜ ሊሆን ይችላል (ከመዝ118፥22-23፤ከኢሳ8፥13-15፤28፥16እና ማብ ይመ፤ ዳን2፥35፡45፤ከማቴ21፥42፤ኤፌ2፥19-22፤ከ1ጴጥ2፥6-8ጋር ያነጻጽሩ)። *ሰባት ዐይኖች፤* መጨረሻ የሌለውን ዕውቀት፣ "ሁሉን ዐዋቂነት" የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (የ4፥10ማብ ይመ)። *የዚህችንም ምድር በደል....አስወግዳለሁ፤* በቍ4 ላይ የተጠቀሰው ትእምርት እዚህ ላይ ተብራርቶአል። "ምድር" የሚለው ቃል የእስራኤልን ሕዝብ ያመለክታል። በዚህ ስፍራ ስለተነገረው 12፥10-13፡1 ይመ። *በአንድ ቀን፤* ጌታ የተሰቀለበትን ዓርብ ቀን የሚያመለክት ነው፤ አንዳንዶች ግን የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ጭምር ያመለክታል ይላሉ።

3፥10፤ *በዚያን ቀን፤* የጌታን ቀን ማለት ነው (2፥11ይመ እንዲሁም የኢሳ 2፥11፡17፡20 ማብ ይመ)። *በግዛ ወይኑና በለሱ ሥር ሆኖ፤* ሰላምን፣ ዋስትናንና እርካታን የሚያመለክት ሥዕላዊ ገለጻ ነው (2ነገ18፥31፤ሚክ4፥4 እና ማብ ይመ)።

4፥1-14፤ የዘካርያስ አምስተኛው ራእይ ነው። አይሁድ የአምላካቸውን መልካምነት ተመልክተው ቤተ መቅደሱን መልሰው እንዲሠሩ የሚያበረታታ ነው። በቤተመቅደሱ ውስጥ ካለው መቅረዝ የሚወጣው ብርሃን የሚወክለው፣ የእግዚአብሔርን ሕዝብና በመንፈስ ቅዱስ ኀይል በሚሰጠው ቅዱስ አገልግሎት የሚገለጸውን የእግዚአብሔርን የክብር መንጸባረቅ ነው (ቍ6፡12፤ የዘፀ25፥31 ማብ ይመ። ይህ ኀይል ዘሩባቤል መቅደሱን መልሶ መሥራት የሚችልበትን ጕልበት ይሰጠዋል (ቍ6-10)። ዘሩባቤል ንጉሣዊውን፣ ኢያሱ ደግሞ የክህነት አገልግሎትን በመወከል ሲያገለግሉ፣ የእግዚአብሔር መንፈስ ለሕዝቡ መቅደሱን መልሰው መሥራት የሚችሉብትን ችሎታ ይሰጣቸዋል (ቍ11-14)።

4፥1፤ *አነቃኝ፤* በዚያው ሌሊት ነው (የ1፥8ማብ ይመ)።

4፥2፤ *ምን ታያለህ?* 5፥2ይመ፤ እንዲሁም ኤር1፥12 እና ማብ ይመ። ምናልባት ይህ ራእይ እንደ ዘይት መያዣ ሆኖ በሚያገለግለው በትልቁ ማሰሮ ዙሪያ ስለ ተደረደሩት ሰባት መብራቶች ነው። "ሰባቱ የመብራት ቧንቧዎች" ዘይቱን ከማሰሮው ወደ መብራቶቹ ይወስዳሉ። ይህ ክፍል ሌላም ትርጕም ሊኖረው ይችላል፤ ይኸውም ቧንቧዎቹ የመብራቱን ክር የሚያስገቡ

# ትንቢተ ሚልክያስ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ጸሐፊው ሚልክያስ እንደ ሆነ ይነገራል፤ የስሙም ትርጉም፣ "መልእክተኛዬ" ማለት ነው:: ይኸው ቃል በ3፥1 ላይ በመገኘቱና ነቢያትም ሆኑ ካህናት፣ የጌታ መልእክተኞች እንደ መሆናቸው (2፥7፤ሐጌ 1፥13 ይመ) አንዳንድ ሰዎች፣ "ሚልክያስ" የሚለውን መጠሪያ ሕዝቡ በልማድ ብቻ ለጸሐፊው የሰጠው ስም ነው ይላሉ:: ለዚህ አመለካከታቸው ዋቢ አድርገው የሚያቀርቡት የጥንቱን የሰብዓ ሊቃናት የግሪክ ትርጒም ነው፤ ምክንያቱም ይህ ትርጒም በ1፥1 ላይ የሚገኘውን የተጸውዖ ስም በማድረግ ፈንታ እንዲሁ "መልእክተኛው" ብሎታል::

### ታሪካዊ ዳራው

ከምርኮ የተመለሱት ወገኖች በሐጌና በዘካርያስ ትንቢታዊ እንቅስቃሴ ተነሣሥተው፣ የቤተ መቅደሱን ሥራ በገዣቸው በዘሩባቤል መሪነት በ516 ዓ.ቅ.ክ አጠናቀቁ:: በ458 ዓ.ቅ.ክ ካህኑ ዕዝራና በሺህ የሚቈጠሩ አይሁድ ከምርኮ በመመለሳቸው ማኅበረሰቡ ተበረታቶአል:: ዕዝራ... የሚካሄደውን አምልኮ ፈርጅ አስይዞ እንዲያዳብረውና (ዕዝ 7፥17) የሙሴም ሕግ በመታዘዝ ሥራ ላይ መዋሉን እንዲያረጋግጥ (ዕዝ 7፥25-26)፣ የፋርሱ የንጉሥ አርጤክስስ ዕዝራን አበረታታው::

ከዐሥራ ሦስት ዓመት በኋላም (445 ዓ.ቅ.ክ)፣ ይኸው የፋርስ ንጉሥ ጠጅ አሳላፊው ነህምያ ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመለስና ቅጥሮቹን እንደ ገና እንዲሠራ ፈቀደለት (ነህ 6፥15):: ነህምያ አዲስ የተሾመ ገዥ እንደ መሆኑ መጠን፣ ድኾች የሚረዱበትን መንገድ በመቀየስ ረገድ ግምባር ቀደም ስፍራን ያዘ (ነህ 5፥12-13)፤ ከዚህም በላይ ከባዕድ ሕዝብ ጋር የሚፈጸመው ጋብቻ ዕርም ተብሎ እንዲቀር፣ ሰንበት እንዲከበር (ነህ 10፥30-31)፣ ዐሥራትና መባቸውንም በታማኝነት እንዲከፍሉ (ነህ 10፥37-39) ሕዝቡን አግባባ::

ነህምያ በ433 ዓ.ቅ.ክ የፋርስን ንጉሥ ለማገልገል ወደዚያ ተመለሰ፤ የአይሁድ ሕዝብም እርሱ በሌለበት ወቅት እንደ ገና በኀጢአት ወደቀ:: ኋላ ግን ነህምያ ወደ ኢየሩሳሌም በተመለሰ ጊዜ፣ ዐሥራት መክፈል እንደ ቀረ፣ ሰንበት እንደ ተሻረ፣ ሕዝቡም ከባዕዳን ሕዝቦች ጋር እንደ ተጋቡና ካህናቱም በምግባረ ብልሹነት እንደ ተበከሉ (ነህ 13፥7-31) ተመለከተ:: ከእነዚህ በደሎች ብዙዎቹን ነቢዩ ሚልክያስ አውግዞአል (1፥6-14፤ 2፥14-16፤ 3፥8-11 ይመ)::

### የተጻፈበት ጊዜ

ነህምያና ሚልክያስ ያወገዟቸው የሕዝቡ በደሎች ተመሳሳይ መሆናቸው፣ ሁለቱም መሪዎች በአንድ ዘመን እንደ ነበሩ ያመክታል:: ትንቢተ ሚልክያስ በ433 ዓ.ቅ.ክ ነህምያ ወደ ፋርስ ከተመለሰ በኋላ ወይም ለሁለተኛ ጊዜ ገዥ ሆኖ በተሾመበት ጊዜ ተጽፎ ሊሆን ይችላል:: ይሁን እንጂ በ1፥8 የተጠቀሰው ገዥ (የዚህኑ ማብ ይመ) ነህምያ ላይሆን ስለሚችል፣ የመጀመሪያው አማራጭ እውነት ላይሆን አይቀርም:: ሚልክያስ የመጨረሻው የብሉይ ኪዳን ነቢይ ላይሆን አይቀርም (አንዳንዶች ግን ኢዩኤልን ከእርሱ በኋላ የተነሣ ነቢይ አድርገው ይቈጥራሉ)::

### የመጽሐፉ መሪ ሐሳብና ትምህርተ መለኮት

አይሁድ ከምርኮ ተመልሰው ቤተ መቅደሱን እንደ ገና እንዲሠሩ ቢፈቅድላቸውም እንኳ፣ አንዳንድ ተስፋ አስቈራጭ ሁኔታዎች በሃይማኖታቸው ላይ ሕጸጽ አስከትለዋል፤ (1) ምድራቸው በፋርስ ሰፊ ግዛት መካከል ተገልላ የተቀመጠች አነስተኛ ክፍለ አገር ሆና ቀርታለች፤ (2) በነቢያቱ (ሌሎች ይደጎሪ ምርኮ ነቢያትን ሐጌንና ዘካርያስን ጨምሮ) የክብር ዘመን ወደፊት እንደሚመጣ የተተነበየው ትንቢት አልተፈጸመም፤ (3) አምላካቸው በመዝ 68 እንደ ተመለከተው በአሕዛብ ፊት መንግሥቱን ከፍ ከፍ ለማድረግ ሲል በኀይልና በግርማ ወደ መቅደሱ አልመጣም (3፥1):: ከዚህም የተነሣ የእግዚአብሔርን የፍቅር ኪዳን በመጠራጠርና (1፥2) በፍትሕ ሰጪነቱ ባለመታመን (2፥17፤ 3፥14-15)፣ ወደ ምድሩ የተመለሰው የአይሁድ ማኅበረ ሰብ ተስፋ መቍረጥ ጀመረ:: አምልኮአቸው ከዘመን ዘመን እንዲሁ የሚዝነበት ሃይማኖታዊ ሥርዐት ብቻ ሆነ፤ ሕጉንም በጥንቃቄ ማክበሩን ገሸሽ አደረጉ::

ሚልክያስ ካህናቱና (1፥6-2፥9) ሕዝቡ (2፥10-16) የእግዚአብሔርን ፍቅር እየተጠራጠሩ (1፥2-5)፣ እምነተ ቢሶች በመሆናቸው ይወቅሳቸዋል::እግዚአብሔር ኢፍትሐዊ ነው፤ ሕዝቡንም ከፍ ከፍ ያደርግ ዘንድ በፍርድ አልመጣም ("የፍርድ አምላክ ወዴት አለ?" 2፥17)፤ በማለት ያቀረቡትን ክስ ሚልክያስ በግልጽ በመናገርና በማስጠንቀቅ ይመልሳቸዋል:: እንዲመጣ የፈለጉት ጌታ በእርግጥ ይመጣል፤ ሆኖም "እንደ አንጥረኛ እሳት" (3፥1-4) ሆኖ ነው:: ለፍርድ መምጣቱ የማይቀር ነው፤ ነገር ግን ፍርዱ በመጀመሪያ በሕዝቡ ላይ ይፈጸማል (3፥5)::

ጌታ የገባውን ቃልና የነደፈውን ዕቅድ እንደ ሰው የማያጥፍና የማይሰርዝ አምላክ በመሆኑ፣

በተደጋጋሚ ከእምነት ያፈነገጠችውን እስራኤልን ጨርሶ አይተዋትም (3፥6)። ይሁን እንጂ፣ እስራኤል የእግዚአብሔርን በረከት እንደ ገና የምታገኘው (3፥6-12)፣ ሕይወቷን በንስሓ ስታድስ ብቻ ነው። ጌታን የሚያከብር ሁሉ እርሱ ለፍርድ በሚመጣበት ጊዜ ከጥፋት ያመልጣሉ (3፥16-18)።

በመደምደሚያም ሚልክያስ እንደ ገና "ያ ታላቅና አስፈሪ ቀን ይመጣል (4፥5)፤ እንደ ምድጃ እሳትም ያቃጥላል" (4፥1) በማለት ለአንባቢዎቹ ያረጋግጥላቸዋል፤ ያስጠነቅቃቸዋልም። በዚያን ቀን ጻድቃን ሐሤት ያደርጋሉ፤ "እናንተም ክፉዎችን ትረግጣላችሁ" (4፥1-3)። ስለዚህ "የባሪያዬን የሙሴን ሕግ ልብ በሉ" (4፥4)። ሕዝቡን ለዚያ ቀን ለማዘጋጀትና ወደ ቀደሙት አባቶቻቸው የጽድቅ መንገድ ለመመለስ ጌታ "ነቢዩን ኤልያስን" ይልካል፤ (4፥5-6)።

## ሥነ ጽሑፋዊ ባሕርያት

ትንቢተ ሚልክያስ፣ "ንግር" ይባላል (1፥1 እና ማብ ይመ)፤ በአጻጻፍ ረገድ ሲታይም ከፍተኛ ደረጃ ያለው የስድ ንባብ ጽሑፍ ነው። በጽሑፉ ውስጥ በእግዚአብሔርና በሰዎች አንደበት የቀረቡ ተከታታይ ጥያቄዎች ጐልተው ይታዩበታል። ብዙው ጊዜ ጌታ ሲናገር፣ "እናንተ ግን እንዲህ ብላችኋል" (1፥2፡6-7፤ 2፥14፡17፤ 3፥7-8፡13 ይመ፤ ከ1፥13 ጋር ያነጻጽሩ) የሚል የምፀት ቃል ይከተለዋል፤ ለእያንዳንዱም ጌታ መልስ ይሰጣል።

ድግግሞሽ የመጽሐፉ ዋና ባሕርይ ነው። "እግዚአብሔር ጸባኦት" የሚለው መጠሪያ ሃያ ጊዜ ተጽፎ ይገኛል። መጽሐፉ የኤዶምያስ ጠፍ ምድር ምን እንደሚመስል በመግለጽ ይጀምርና (1፥3-4)፣ እስራኤል ጥፋት እንዳይደርስባት በማስጠንቀቅ ይደመድማል (4፥6)።

በትንቢተ ሚልክያስ ውብ አባባሎች በብዛት ይገኛሉ። ካህናቱ በጌታ መሥዋዕት ላይ በንቀት ጢቅ አለብት (1፥13)፤ ጌታም መሥዋዕታቸውን ፋንድያ በፊታቸው ላይ ይበትናል (2፥3)። ጻድቅ ፈራጅ እንደ መሆኑ መጠንም፣ "እንደ አንጥረኛ እሳትና እንደ አጣቢ ሳሙና ይሆናል" (3፥2)፤ ለጻድቃን ግን "የጽድቅ ፀሐይ በክንፎቿ ፈውስን አዝላ ትወጣለች፤ እናንተም ወጥታችሁ ከጋጡ እንደ ተለቀቀ ጥጃ ትፈነጫላችሁ" (4፥2)።

## አስተዋፅኦ

1. ርእስ (1፥1)
2. መግቢያ፤ እግዚአብሔር ለእስራኤል ያለው የኪዳን ፍቅሩ መረጋገጡ (1፥2-5)፤
3. እስራኤል ታማኝ ሆና ባለመገኘቷ ተግሣጽ ደረሰባት (1፥6-2፥16)

ሀ. የካህናቱ ታማኝ አለመሆን (1፥6-2፥9)
  (1) በመሥዋዕታቸው እግዚአብሔርን አላከበሩም (1፥6-14)
  (2) ሕጉን በታማኝነት አላስተማሩም (2፥1-9)

ለ. ሕዝቡ ታማኝ ሆነው አለመገኘታቸው (2፥10-16)

4. የጌታ መምጣት መታወጁ (2፥17-4፥6)

  ሀ. ጌታ ካህናቱን ለማንጻትና በሕዝቡ ላይ ለመፍረድ ይመጣል (2፥17-3፥5)።
  ለ. ከጌታ መምጣት አንጻር ሕዝቡ ንስሓ እንዲገባ የቀረበ ጥሪ (3፥6-18)
    (1) የሕዝቡ ስጦታ በታማኝነት እንዲሆን የተሰጠ ምክር (3፥6-12)
    (2) ሕዝቡ በታማኝነት እንዲያገለግል የተሰጠ ምክር (3፥13-18)

ሐ. የጌታ ቀን መምጣት አይቀሬ መሆኑ በግልጽ ተናገረ (ም 4)

**1** በሚልክያስ[ህ] በኩል ወደ እስራኤል የመጣው የእግዚአብሔር ቃል ንግር ይህ ነው፤

## ያዕቆብ ተወደደ፤ ዔሳው ተጠላ

[2]"እኔ ወድጃችኋለሁ" ይላል እግዚአብሔር፤ "እናንተ ግን፣ 'እንዴት ወደድኸን?' ትላላችሁ።

እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፤ "ዔሳው የያዕቆብ ወንድም አልነበረምን? ያዕቆብን ወደድሁት፤ [3]ዔሳውን ግን ጠላሁት፤ ተራሮቹን ባድማ አደረግሁ፤ ርስቱንም ለምድረ በዳ ቀበሮዎች ሰጠሁበት።"

[4]ኤዶምያስ፣ "ብንደመሰስም እንኳ የፈረሰውን መልሰን እንሠራዋለን" ይል ይሆናል። እግዚአብሔር ጸባኦት ግን እንዲህ ይላል፤ "እነርሱ ይሠሩ ይሆናል፤ እኔ ግን አፈርሳቸዋለሁ፤ ክፉ ምድር፣ እግዚአብሔርም ለዘላለም የተቈጣው ሕዝብ ተብለው ይጠራሉ። [5]ይህንም በገዛ ዐይናችሁ ታያላችሁ፤ እናንተም፣ 'ከእስራኤል ዳርቻ ወዲያ እንኳ እግዚአብሔር ታላቅ ነው!' ትላላችሁ።

## እንከን ያለበት መሥዋዕት

[6]"ልጅ አባቱን፣ ባሪያም ጌታውን ያከብራል፤ እኔ አባት ከሆንሁ፣ መከበሬ የት አለ? ጌታስ ከሆንሁ መፈራቴ የት አለ? ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፤ "ካህናት ሆይ፤ ስሜን የምታቃልሉት እናንተ ናችሁ።

"እናንተ ግን፣ 'ስምህን ያቃለልነው እንዴት ነው?' ትላላችሁ።

[7]"በመሠዊያዬ ላይ የረከሰ ምግብ ታስቀምጣላችሁ።

"እናንተ ግን፣ 'ያረከስንህ እንዴት ነው?' አላችሁ።

"የእግዚአብሔር ገበታ የተናቀ ነው በማለታችሁ ነው። [8]የታወረውን እንስሳ ለመሥዋዕት ስታቀርቡ፣ ያ በደል አይደለምን? አንካሳውን ወይም በሽተኛውን እንስሳ መሥዋዕት አድርጋችሁ ስታቀርቡ፣ ያስ በደል አይደለምን? ያንኑ ለገዢችሁ ብታቀርቡ፣ በእናንተ ደስ ይለዋልን? ወይስ ይቀበለዋልን?" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

[9]"አሁን ግን እንዲራራልን እግዚአብሔርን ለምኑ፤ እንደዚህ ዐይነቱን መሥዋዕት ይዛችሁ ስትቀርቡ ይቀበላችኋልን?" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት። [10]"በመሠዊያዬ ላይ ከንቱ እሳት እንዳታነዱ፣ ምነው ከእናንተ አንዱ የቤተ መቅደሱን ደጅ በዘጋ ኖሮ! እኔ በእናንተ ደስ አይለኝም፤ ከእጃችሁም ምንም ዐይነት ቍርባን አልቀበልም" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት። [11]ከፀሐይ መውጫ ጀምሮ እስከ መግቢያዋ ድረስ፣ ስሜ በሕዝቦች መካከል የከበረ ይሆናል፤ በየስፍራውም ሁሉ ለስሜ ዕጣንና ንጹሕ ቍርባን ያቀርባሉ፤ ስሜ በሕዝቦች መካከል የከበረ ይሆናልና" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

[12]"እናንተ ግን የእግዚአብሔር ገበታ፣ 'ርኩስ ነው' ምግቡም፣ 'የተናቀ ነው' በማለት ታቃልላላችሁ። [13]ደግሞም፣ 'ይህ ድካም ነው' በማለት በንቀት ጢቅ አላችሁበት ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

"በቅሚያ የመጣውን፣ አንካሳውንና የታመመውን እንስሳ ቍርባን አድርጋችሁ ስታቀርቡ ከእጃችሁ መቀበል ይገባኛልን?" ይላል

1፥1 ናሆ1፥1፤ ሐሥ7፥38፤ ሮሜ3፥1-2፤1ጴ4፥11
1፥2 ቍ6፥7፤ዘዳ4፥37፤ ኤር46፥27፤ሚል2፥14፤ 17፤3፥7፥13፤ሮሜ9፥13
1፥3 ኢሳ13፥22፤ 34፥10፤ሉቃ14፥26
1፥4 ኢሳ9፥10፤ 11፥14፤34፥5፥11፤ ሰቆ4፥22፤ ሕዝ25፥12-4፤26፥14
1፥5 መዝ35፥27፤ 48፥1፤ኢሳ45፥22፤ 52፥10፤አሞ1፥11-12፤ ሚክ5፥4
1፥6 ቍ2፤ዘሌ20፥9፤ ዘዳ31፥12፤ኢዮ5፥17፤ ኢሳ1፥2፤ማቴ15፥4፤ 23፥9፤ሉቃ6፥46
1፥7 ቍ2፥12፤ ዘሌ21፥6፤ሕዝ23፥41
1፥8 ዘፍ32፥20፤ ዘሌ1፥3፤ዘዳ15፥21፤ ኢሳ43፥23
1፥9 ዘሌ23፥33፥44፤ መዝ51፥17፤ኤር6፥20፤ ሚክ6፥6–8፤ ሮሜ12፥1፤ ዕብ13፥16
1፥10 ቍ13፤ ዘሌ22፥20፤ 2ዜና28፥24፤ ኢሳ1፥11-14፤ ኤር14፥12፤ሆሴ5፥6፤ ሚል2፥12
1፥11 መዝ113፥3፤ ኢሳ6፥3፤12፥4፤ 19፥21፤24፥15፤ 56፥6፤60፥6-7፤ ማቴ8፥11፤ዕብ13፥15፤ ራእ5፥8፤8፥3
1፥12 ቍ7፤ሕዝ41፥22
1፥13 ቍ10፤ ዘኍ14፥11፤ዘዳ15፥2

1፤ኢሳ43፥22-24
[ህ]1 ሚልክያስ የስሙ ትርጒም መልእክተኛዬ ማለት ነው።

1፥1 *ንግር*፤ ዘካ 9፥1 እና ማብ ይመ 12፥1 እንዲሁም ዕን 1፥1 እና ማብ ይመ።

1፥2 *ወድጃችኋለሁ*፤ እግዚአብሔር ተስፋ ለቈረጠው ለእርሱ ሕዝብ የሰጠው ማረጋገጫ ነው።

1፥3 *ዔሳውን...ጠላሁት*፤ እስራኤል በእግዚአብሔር የቃል ኪዳን ፍቅሩ ላይ ጥርጣሬ የሚያድርበት ከሆነ፣ እግዚአብሔር ከእርሷዋ ጋር ያለውን ሁኔታ የያዕቆብ ወንድም ከሆነው ከዔሳው (ከኤዶም) ጋር ካለው ሁኔታ ጋር ማነጻጸር ይኖርበታል። ጳውሎስ፣ እግዚአብሔር ለያዕቆብ ያለውን ፍቅር፣ በዔሳው ላይ ካለው ጥላቻ ጋር በማነጻጸር ከምርጫ አኳያ አብራርቶታል (ሮሜ 9፥10-13)። እግዚአብሔር ያዕቆብን እንጂ ዔሳውን አልመረጠውም። እዚህ ላይ "መውደድ" እና "ጥላቻ" የሚሉት ቃላት እንዴት ጥቅም ላይ እንደዋሉ ያዕቆብ ራሔልን አብልጦ ከመውደዱና ልያን ከመጥላቱ ጋር ያነጻጽሩ (ዘፍ 29፥31፡33 ከዘዳ 21፥16-17 ጋር ያነጻጽሩ)። አማኞችም በዚህ ሁኔታ ከወላጆቻቸው ይልቅ (ሉቃ 14፥26) ክርስቶስን አብልጠው መውደድ ይገባቸዋል ማቴ 10፥37። *ባድማ*፤ ሚልክያስ እዚህ ላይ ስለ ኤዶም የተናገረው፣ ከእርሱ በፊት የነበሩት ነቢያት የተናገሩትን የሚያስተጋባ ነው (ኢሳ 34፥5-15፤ ኤር 49፥7-22፤ሕዝ25፥12-14፤35፥1-15፤ አብድዩ ይመ)።ከ550-400 ዓ.ቅ.ክ ባለው ጊዜ ውስጥ የናባጢያን ዐረቦች ኤዶማውያንን ቀስ በቀስ አስለቅቀዋቸዋል።

1፥4፤*ኤዶምያስ...ይል ይሆናል*፤ ከትዕቢቷ የተነሣ በራሷ ብትመካም ይህ ለደኅንነቷ ዋስትና አልሆናትም፤ የወደፊት ዋስትናዋንም አያረጋግጥላትም (ከኤር 49፥16 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥5 *ከእስራኤል...ታላቅ*፤ ተጠራጣሪዋ እስራኤል የኤዶም የመጨረሻ ዕጣ ፈንታ በምታይበት ጊዜ፣ እግዚአብሔር አሕዛብን ሁሉ የሚገዛ ታላቅ አምላክ መሆኑን አምና ትቀበላለች።

*1፥6-2፥9*፤ እግዚአብሔር ካህናትን የገሠጸበት ክፍል ነው።

1፥6 *ልጅ አባቱን...ያከብራል*፤ ከኢሳ 1፥2-3 ጋር ያነጻጽሩ። ካህናት...ስሜን የምታቃልሉት፤ ከ2፥5 ጋር ያነጻጽሩ እንዲሁም ኢሳ 1፥4 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥7 *ምግብ*፤ መሥዋዕት ማለት ነው (ቍ12፤ ዘሌ21፥8፡21ይመ)። *ያረከስንህ*፤ የረከሰ መሥዋዕት በማቅረብ እግዚአብሔርን ራሱን አርክሰውታል። *የእግዚአብሔር ገበታ*፤ መሠዊያ ማለት ነው (ቍ12፤ሕዝ44፥16 ይመ)። ካህናቱ የሚበሉት ከመሥዋዕቱ ላይ ወስደው ስለሆነ፣መሠዊያው ምግባቸውን የሚያገኙበት ገበታ ነው። *የተናቀ*፤ አድርገው የእግዚአብሔርን መሠዊያና መሥዋዕቱን የተናቀ ነው ብለው እስከቈጠሩ ድረስ (ቍ12)፣ እግዚአብሔርም እነርሱን በሕዝቡ ዘንድ እንዲናቁ ያደርጋቸዋል (2፥9እናማብ ይመ)።

1፥8 *የታወረውን...አንካሳውን*፤ አካለ ጐደሎ የሆኑ ወይም እንከን ያለባቸውን እንስሳትን እግዚአብሔር ለመሥዋዕትነት አይቀበላቸውም (ዘዳ 15፥21)። *ለገዢችሁ*፤ ምናልባት የፋርስን ገዦች ማለቱ ሳይሆን አይቀርም።

1፥10 *የቤተ መቅደሱን ደጅ በዘጋ*፤ የተናቀ መሥዋዕት ከማቅረብ ጨርሶ መሥዋዕት አለማቅረቡ ይመረጣል (ከኢሳ 1፥11-15 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥11 *በሕዝቦች መካከል የከበረ*፤ ከቍ 14 ጋር ያነጻጽሩ። የእግዚአብሔር ፍርድ በኤዶምና በሌሎች አሕዛብ ላይ ሲሆን፣ በአማልክቶቻቸው ላይ የእግዚአብሔር ታላቅነት ይገለጣል፤ በዚህም የእርሱን ማንነት እንዲገነዘቡ ያደርጋቸዋል (ሶፎ2፥11 ይመ)። *ዕጣንና ንጹሕ ቍርባን*፤ በኢሳ56፥6-7፤60፥7 መጻተኞች የሚያቀርቡትን መሥዋዕት እግዚአብሔር እንደሚቀበለው ከሚናገረው ክፍል ጋር ያነጻጽሩ፤ አንዳንድ ሰዎች "ዕጣን" ማለት "ጸሎት" ማለት ነው ይላሉ (ከራእ 5፥8 ጋር ያነጻጽሩ)፤ "መሥዋዕት" የሚለውን "ውዳሴ" (ከዕብ13፥15ጋር ያነጻጽሩ) ማለት ነው ይላሉ።

1፥12፤ *የተናቀ...ታቃልላላችሁ*፤ቍ7 ይመ።

1፥13፤ በንቀት ጢቅ አላችሁበት፤ በ1ሳሙ 2፥15-17 ላይ

እግዚአብሔር፤ [14]"በመንጋው ውስጥ ተቀባይ ነት ያለው ተባዕት በግ ኖሮት ይህንኑ ሊሰጥ ተስሎ ሳለ በማታለል ነውር ያለበትን እንስሳ በጌታ የሚሠዋ ርጉም ይሁን፤ እኔ ታላቅ ንጉሥ ነኝ፤ ስሜም በሕዝቦች ዘንድ ሊፈራ የሚገባ ነውና" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፡፡

## ለካህናት የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

**2** "አሁንም ካህናት ሆይ፤ ይህ ማስጠንቀቂያ ለእናንተ የተሰጠ ነው፤ [2]ባትሰሙ፣ ልባችሁንም ስሜን ለማክበር ባታዘጋጁ፣ ርግማን እሰድባችኋለሁ፤ በረከታችሁንም ወደ መረገም እለውጠዋለሁ፤ ልታከብሩኝ ልባችሁን አላዘጋጃችሁምና' ረግሜዋለሁ ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፡፡

[3]"ዘራችሁን[a] እገሥጻለሁ[b]፤ የመሥዋታችሁን ፋንድያ በፊታችሁ ላይ እበትናለሁ፤ እናንተም ከእርሱ ጋር ትወገዳላችሁ፤ [4]ከሌዊ ጋር የገባሁት ኪዳን ይጸና ዘንድ፣ ይህን ማስጠንቀቂያ የላክሁት እኔ መሆኔንም ታውቃላችሁ" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፡፡ [5]"ከእርሱ ጋር የገባሁት ኪዳን የሕይወትና የሰላም ኪዳን ነበር፤ እነርሱንም ሰጠሁት፤ ይህም ክብርን አመጣ፤ እርሱም አከበረኝ፤ ስሜንም በመፍራትም ጸና፡፡ [6]እውነተኛ ትምህርት በአፉ ነበር፤ ምንም ዐይነት የሐሰት ነገር በአንደበቱ አልተገኘም፤ ከእኔ ጋር በሰላምና በቅንነት ተራመደ፤ ብዙዎችንም ከኀጢአት መለሰ፡፡

[7]"ካህኑ የሁሉ ገዥ፣ የእግዚአብሔር መልእክተኛ ስለ ሆነ ከንፈሮቹ ዕውቀትን ሊጠብቁ፣ ሰዎችም ከአንደበቱ ትምህርትን ሊፈልጉ ይገባል፤ [8]እናንተ ግን ከመንገዱ ወጥታችኋል፤ በትምህርታችሁም ብዙዎች እንዲሰናከሉ አድርጋችኋል፤ የሌዊንም ኪዳን አፍርሳችኋል" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት፡፡ [9]"ስለዚህ በመንገዴ ስላልሄዳችሁና በትምህርታችሁም አድልዎ ስላደረጋችሁ፣ በሰዎች ሁሉ ፊት እንድትናቁና እንድትዋረዱ አድርጌአችኋለሁ፡፡"

## የይሁዳ አለመታመን

[10]ሁላችን አንድ አባት ያለን አይደለን ምን? የፈጠረንስ አንድ ስምባክ አይደለምን? ታዲያ እርስ በርሳችን ታማኝነት በማጉደል የአባቶቻችንን ኪዳን ለምን እናረክሳለን? [11]ይሁዳ አልታመነም፤ በእስራኤልና በኢየሩሳሌምም አስጸያፊ ነገር ተፈጽሞአል፤ ይሁዳ የባዕድ አምላክ ሴት ልጅ በማግባት እግዚአብሔር የሚወደውን መቅደስ አርክሶአል፡፡ [12]ይህን የሚያደርግ ማንኛውም ሰው ቢሆን፣[c] ለእግዚአብሔር ጸባኦት ቍርባን ቢያመጣም እንኳ፣ እግዚአብሔር ከያዕቆብ[c] ድንኳን ያስወግደው፡፡

[13]ሌላው የምታደርጉት ነገር ደግሞ፣ የእግዚአብሔርን መሠዊያ በእንባ ታጥለቀልቃላችሁ፤ ከእንግዲህ ወዲያ ቍርባናችሁን ስለማይመለከትና በደስታም ከእጃችሁ

1፥14 ዘፀ12፥5፤ ዘሌ22፥18-21፤ ዘዳ28፥58፤ መዝ72፥8-11፤95፥3፤ ኤር46፥18፤አብ1፥21፤ 1ጢሞ6፥15
2፥1 ቍ7
2፥2 ዘኍ6፥23-27፤ ዘዳ11፥26፤28፥20፤ ኤር13፥17፤ምዕ15፥7-9፤ ዮሐ5፥23፤1ጢሞ6፥16፤ ራእ5፥12-13
2፥3 ዘፀ29፥14፤ ዘሌ4፥11፤1ነገ14፥10፤ ኢዮ9፥31
2፥4 ዘኍ3፥12
2፥5 ዘኍ25፥12፤ ዘዳ14፥23፤28፥58፤3 3፥9፤መዝ25፥10፤10 3፥18፤119፥161፤ ማቴ26፥28፤ሉቃ22፥ 20፤ዕብ7፥22፤12፥28
2፥6 ዘፍ5፥22፤ ዘዳ33፥10፤መዝ25፥21፤ ሉቃ2፥14፤ዮሐ14፥27፤ ሮሜ11፥14፤ገላ5፥22፤ ያዕ5፥19-20
2፥7 ዘሌ10፥11፤ ዘኍ27፥21፤ 2ዜና17፥7፤36፥15፤ ኤር18፥18፤ ማቴ11፥10፤ማር1፥2
2፥8 ዘፀ 32፥8፤ኤር2፥8፤ 18፥15፤33፥21፤ ሕዝ22፥26፤ሆሴ4፥6
2፥9 ዘፀ18፥16፤ ዘሌ19፥15፤1ሳሙ2፥ 17፡30፤መዝ22፥6፤ 35፥4፤ኤር3፥25፤ 51፥37፤ሐሥ8፥32-33፤ 10፥34፤ሮሜ2፥11
2፥10 ዘፀ4፥22፤ 19፥5፤2ነገ17፥15፤ ኢዮ4፥17፤ ኢሳ43፥1፤ ኤር31፥32፤ ሰፎ3፥3-4፤ማቴ5፥16፤6፥4፡18፤ሉቃ11፥2፤1ቆሮ8፥6
2፥11 ዘፀ34፥16፤ ዘዳ4፥37፤ ነህ13፥23፤ኢሳ1፥13፤ 48፥8፤ኤር3፥7-9
2፥12 ዘኍ24፥5፤ 1ሳሙ2፥30-33፤2ሳሙ20፥1፤ሕዝ24፥21፤፤ ሚል፤1፥10
2፥13 መዝ39፥12፤ 66፥18፤ኢሳ58፥2፤ ኤር11፥11፤14፥12

[a]3 ወይም እህላችሁ እንዲጠወልግ አደርጋለሁ፡፡
[b]3 ወይም እቈርጣለሁ፤ የሰብዓ ሊቃናትን ትርጕም ይመ፡፡
[c]12 ወይም ይህን ለሚያደርግ ሰው በመልካም የሚመሰክር ማንም ቢኖር፣ እግዚአብሔር ከያዕቆብ ድንኳን ይቍረጠው፡፡

ከተገለጸው የዔሊን ልጆች ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ፡፡ *እንካሳውንና... የታመመውን*፤ ቍ 8 እና ማብ ይመ፡፡

1፥14፤ *ተስሎ.. ነውር ያለበትን*፤ ስእለትን ለማድረስ መሥዋዕት ሆኖ የሚቀርብ እንስሳ ነውርና ነቀፋ የሌለበት መሆን ይገባዋል (ዘሌ22፥18-23ይመ)፡፡ *ታላቅ ንጉሥ*፤ ዘካ14፥9 ይመ፡፡ ስሜም...የሚፈራ ነውና፤ በቍ 8 ላይ ከተጠቀሰው ገዥ ይበልጥ ለማለት ነው (ቍ11እና ማብ ይመ)፡፡

2፥2 *በረከታችሁንም ወደ መርገም*፤ በሕዝቡ ላይ የበረከትን ቃል መናገር የካህናት ድርሻ ነው (ዘኍ 6፥23-27 ይመ)፤ ሆኖም ግን መባረካቸው ርግማን ከሆነ፣ የእነርሱ ድርሻ ብቻ የሆነው የክህነት አገልግሎት ከንቱና ይሆናል፡፡

2፥3 *በፊታችሁ ላይ እበትናለሁ*፤ እንዲዋረዱ ለማድረግ ነው፡፡ ናሆ3፥6 ይመ፡፡ *ፋንድያ*፤ ከጋማ ከብት የሚወጣ አዛባ ወይም የዚህ ስብስብ ቈሻሻ፡፡

2፥4 *ከሌዊ*፤ ካህናት የተመረጡት ከሌዊ ነገድ ነው (ዘኍ3፥12-13፤ነህ13፥29)

2፥5 *የሕይወትና የሰላም ኪዳን*፤ ከአሮን የልጅ ልጅ ከፊንሐስ ጋር የተደረገውን ኪዳን ቀጥታ ባልሆነ መንገድ የሚያመለክት ነው፡፡ (ዘኍ25፥10-13ይመ)፡፡ ፊንሐስ ከብዔልፌጎር ጋር የተያያዘ የጣዖት አምልኮና ዝሙት የፈጸሙትን ሁለት ሰዎች በመግደል፣ የእግዚአብሔርን ክብር አስጠብቆአል (ዘኍ 25፥1-3)፡፡ *አከበረኝ*፤ ፊንሐስ ይህን ያሳየው ለእግዚአብሔር ባለው ቅናት ነው (ዘኍ25፥13 ይመ)፡፡

2፥6-7 *ትምህርትን*፤ ካህናት የሙሴን ሕግ የማስተማር ኀላፊነት አለባቸው (ዘሌ 10፥11፤ የሰፎ 3፥4፤ ሐጌ2፥11 ማብ ይመ)፡፡

2፥6 *በሰላምና በቅንነት*፤ እነዚህ ቃላት በመዝ37፥37 ላይም ተያይዘው ገብተዋል፤ እዚህ ላይ ግን "ከእኔ ጋር በሰላምና በቅንነት ተራመደ" የሚለው ዐረፍተ ነገር የሚያመለክተው ለኪዳኑ ያለውን ታማኝነት ነው፡፡

2፥7 *መልእክተኛ*፤ የሕጉ አስተማሪ በመሆኑና በእርሱም አማካይነት ሕዝቡ *የእግዚአብሔርን ፈቃድ* የሚጠይቅ ስለሆነ (የ3፥1 ሐጌ 1፥13 ማብ ይመ)፡፡

2፥8...*ኪዳን አፍርሳችኋል*፤ ታማኝነት በጐደለው ማስተማር፤ እንዲሁም ከአሕዛብ ጋር በጋብቻ በመተሳሰራቸው ምክንያት ሊሆን ይችላል (ዕዝ 9፥1፤10፥18-22፤ነህ13፥27-29 ይመ)፡፡ ከሌዊ ጋር፤ ቍ 4 እና ይመ፤ የ5ን ማብ ይመ፡፡

2፥9 *እንድትናቁና*፤ በዕብራይስጡ ይኸው ቃል በ1፥7፤12 የ1፥7 ማብ ይመ) ላይ "የተናቀ" ተብሎ ተተርጕሞአል፡፡ *አድልዎ ስላደረጋችሁ*፤ ይህ በዘሌ19፥15 ላይ ተከልክሎአል፡፡ በዚህ ረገድ ካህናት እግዚአብሔርን መምሰል ይገባቸው ነበር (ዘዳ 10፥17 ይመ)፡፡

2፥10-16፤ ሚልክያስ "ታማኝነትን ማጉደል" በሚል ሐረግ ሕዝቡን ይገሥጻቸዋል፡፡ ኀጢአታቸውን በተመለከተም በምሳሌነት የሚጠቅሳቸው፤ ሁለት ነገሮች፣ የአሕዛብን ሴቶች ማግባት አንደኛው ሲሆን ፍች ደግሞ ሌላው ነው፡፡

2፥10 *አንድ አባት*፤ ኢሳ 63፥16 ይመ፡፡ *የፈጠረንስ*፤ የተለየ ሕዝቡ አድርጎ ማለት ነው (ኢሳ 43፥1 እና ማብ ይመ)፡፡ *የአባቶቻችንን ኪዳን*፤ እግዚአብሔር ከቀደሙት አባቶቻቸው ጋር በሲና ተራራ ላይ የገባውን ቃል ኪዳን ማለት ነው፡፡ *ታማኝነትን በማጉደል*፤ አንድ ሰው የራሱ ወገን የሆኑትን እስራኤላውያንን እንዲሁም እንደ ካህናት ያሉ አገር መሪዎችን እንኳ ማመን ተስኖት ነበር፡፡

2፥11 *የባዕድ አምላክ ሴት ልጅ*፤ የአሕዛብን ሴቶች ማለት ነው፤ ከአሕዛብ ሴቶች ጋር የሚደረገው እንዲህ ዐይነቱ፣ ጋብቻ ወደ ክህደት የሚወስድ በመሆኑ በኪዳኑ ሕግ አጥብቆ የተከለከለ ነው (ዘፀ34፥15-16፤ዘዳ7፥3-4፤1ነገ11፥1-6 ይመ) እንዲሁም ከኢሱ23፥12-13 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡ ዕዝራና ነህምያም ይህን ችግር በጽኑ ታግለውት ነበር (ዕዝ 9፥1-2፤ነህ 13፥23-29)፡፡

2፥12 *ከያዕቆብ ድንኳን*፤ ማኅበረ ሰቡን የሚያመለክት ዘይቤያዊ ገለጻ ነው፡፡

ስለማይቀበል ታለቅሳላችሁ፤ ትጮኻላችሁም። [14]እናንተም፣ “ለምን ይህ ሆነ?” ብላችሁ ትጠይቃላችሁ። ይህ የሆነው የትዳር ጓደኛህን፣ አጋርህንና የቃል ኪዳን ሚስትህን፣ አታለሃታልና እግዚአብሔር በአንተና በወጣትነት ሚስትህ መካከል ላለው ቃል ኪዳን ምስክር ስለ ሆነ ነው።

[15]እግዚአብሔር አንድ አላደረጋቸውምን? በሥጋም በመንፈስም የእርሱ ናቸው። ለምን አንድ አደረጋቸው? ፈሪሀ እግዚአብሔር ያለው ዘር ይፈልግ ስለ ነበር ነው። ስለዚህ በመንፈሳችሁ ራሳችሁን ጠብቁ፤ ከወጣትነት ሚስታችሁም ጋር ያላችሁን ታማኝነት አታጓድሉ።

[16]“ፍችን እጠላለሁ” ይላል የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር ፤ ልብሱን በግፍ ድርጊት የሚሸፍነውንም ሰው[b] እጠላለሁ” ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

ስለዚህ በመንፈሳችሁ ራሳችሁን ጠብቁ፤ ታማኝነታችሁም አይጓደል።

## የፍርድ ቀን

[17]እግዚአብሔርን በቃላችሁ አታክታችሁታል።

እናንተም፣ “ያታከትነው እንዴት ነው?” ትላላችሁ?

“ክፉ የሚያደርግ ሁሉ በእግዚአብሔር ፊት መልካም ነው፤ እርሱም በክፉዎች ደስ ይለዋል” ወይም “የፍትሕ አምላክ ወዴት ነው?” በማለታችሁ ነው።

**3** “እነሆ፤ በፊቴ መንገድ እንዲያዘጋጅ መልእክተኛዬን እልካለሁ፤ የምትፈልጉት ጌታ በድንገት ወደ ቤተ መቅደሱ ይመጣል፤ ደስ የምትሰኙበትም የቃል ኪዳኑ መልእክተኛ ይመጣል” ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

[2]እርሱ የሚመጣበትን ቀን ማን ሊቋቋመው ይችላል? በሚገለጥበትስ ጊዜ በፊቱ መቆም የሚችል ማን ነው? እርሱ እንደ አንጥረኛ እሳት ወይም እንደ ልብስ አጣቢ ሳሙና ነውና። [3]ብርን እንደሚያነጥርና እንደሚያነጻ ሰው ይቀመጣል፤ ሌዋውያንንም አንጽቶ እንደ ወርቅና እንደ ብር ያጠራቸዋል፤ ከዚያም እግዚአብሔር ቍርባንን በጽድቅ የሚያቀርቡ ሰዎች ይኖሩታል፤ [4]በዚያ ጊዜ የይሁዳና የኢየሩሳሌም ቍርባን እንዳለፉት ቀናትና እንደ ቀድሞው ዘመን እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ ይሆናል።

[5]“ስለዚህ እኔ ለፍርድ ወደ እናንተ እመጣለሁ፤ በመተተኞች፣ በአመንዝራዎች፣ በሐሰት በሚምሉ፣ የሠራተኞችን ደመወዝ በሚከለክሉ፣ መበለቶችንና ድኻ አደጉን በሚጨቍኑ፣ መጻተኞችን ፍትሕ በሚነፍጉ፣ እኔንም በማይፈሩት ላይ እመሰክርባቸው ዘንድ እፈጥናለሁ” ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

## እግዚአብሔርን መስረቅ

[6]“እኔ እግዚአብሔር አልለወጥም፤ ስለዚህ እናንተ የያዕቆብ ልጆች ሆይ፤ አልጠፋችሁም። [7]ከአባቶቻችሁ ዘመን ጀምሮ ከትእዛዛቴ ፈቀቅ ብላችኋል፤ አልጠበቃችኋቸውምም፤ ወደ እኔ ተመለሱ፤ እኔም ወደ እናንተ እመለሳለሁ”

2፥14 ዘፍ21፥30፤ ኢሱ24፥22፤ ምሳ5፥18፤ሕዝ16፥8፤ ሚል1፥2፤ዕብ13፥4
2፥15 ዘፍ2፥24፤ ዘዳ4፥15፤14፥2፤ ኢሳ54፥6፤ ማቴ19፥4-6፤ 1ቆሮ7፥10፡14፤ ዕብ13፥4
2፥16 ዘፍ6፥11፤ 34፥25፤ዘዳ24፥1፤ መዝ51፥10፤ምሳ4፥17፤ ማቴ5፥31-32፤19፥4-9፤ ማር10፥4-5
2፥17 ዘፍ18፥25፤ ኢዮ8፥3፤መዝ5፥4፤ ኢሳ1፥14፤ ሕዝ18፥25፤ሚል1፥2
3፥1 ዘኍ27፥21፤ 1ሳሙ9፥20፤ 2ዜና36፥15፤ኢሳ40፥3፤ 42፥6፤ ሚክ5፥2 ማቴ3፥3፤11፥10፤ ማር1፥2፤ሉቃ7፥27
3፥2 1ሳሙ6፥20፤ ኢዮ9፥30፤ኢሳ1፥31፤ 30፥30፤ሕዝ7፥7፤ 22፥14፤ዳን7፥13፤ ኢል2፥31፤ዘካ13፥9፤ ማቴ3፥10-12፤ 16፥27፤ያዕ5፥8፤2ጴጥ 3፥4፤ራእ1፥7፤6፥17
3፥3 1ዜና23፥28፤ ኢዮ28፥1፤መዝ12፥6፤ 132፥9፤ኢሳ1፥25፤ ዳን12፥10፤1ቆሮ3፥13፤ 1ጴጥ1፥7፤ራእ3፥18
3፥4 2ዜና7፥3፡ 12፤መዝ51፥19፤ ሕዝ20፥40፤ሚል1፥11
3፥5 ዘፀ7፥11፤ 20፥14፤22፥21፡ 22፤ዘሌ19፥11- 12፡13፤ዘዳ24፥19፤ 31፥12፤ኢሳ1፥2፤47፥9፤ ኤር7፥9፤ሕዝ22፥7፤ያዕ2፥11፤5፥4፤ 2ጴጥ2፥12-14
3፥6 ዘኍ23፥19፤ ኢዮ34፥15፤ ሆሴ11፥9፤ ዕብ7፥21፤ ይዕ1፥17

[a]15 ወይም “ነገር ግን አባታችን በሕይወት እስከ ኖረበት ዘመን ድረስ ይህን አላደረገም። ምን ይፈልግ ነበረ? ይፈልግ የነበረው ከእግዚአብሔር ዘንድ ልጅ ለማግኘት ነበረ።
[b]16 ወይም ሚስቱ እንደ ማለት ነው።

2፥13 *ታለቅሳላችሁ፤ ትጮኻላችሁም፤* እግዚአብሔር መሥዋዕታቸውን ስለማይባርክላቸው፣ ድምጻቸውን ከፍ አድርገው ያለቅሳሉ።

2፥14 *የቃል ኪዳን ሚስትህን...ምስክር፤* ጋብቻ ቃል ኪዳን ነው። (ምሳ2፥17 ሕዝ16፥8 ይመ)። ቃል ኪዳንም በምስክሮች ፊት ይጸናል (የዘዳ30፥19፤1ሳሙ20፥23፤ኢሳ8፥1-2 ማብ ይመ)።

2፥15 *አንድ፣* ዘፍ 2፥24 እና ማብ ይመ። *ፈሪሀ እግዚአብሔር ያለውን ዘር፤* ጋብቻ ልጆችን “ይቀድሳል” (1ቆሮ7፥14 እና ማብ ይመ)።

2፥16 *ፍችን እጠላለሁ፤* ኢሳ 50፥1 እና ማብ ይመ። *በግፍ፤* 3፥5 ይመ።

2፥17-4፥16፤ እግዚአብሔር ወደ ሕዝቡ እንደሚመጣ ሚልክያስ የተናገረው ትንቢት የሁለተኛው ክፍል አጋማሽ ነው። ሃይማኖትን በተመለከተ አሉታዊ አመለካከት ስላላቸው እንዲሁም በምግባረ ብልሹነታቸው እግዚአብሔርን አድክመውት ስለ ነበር፣ የእግዚአብሔር ወደ ሕዝቡ የሚመጣው ለፍርድ፣ ለማንጻትና ለመቤዠት ነው።

2፥17 እግዚአብሔርን በቃላችሁ፤ አታክታችሁታል፤ በኢሳ 43፥24 ላይ የእስራኤል ኀጢአት እግዚአብሔርን እንዳደከመው ተጽፎአል። *ክፉ የሚያደርግ ሁሉ...መልካም ነው፤* የአሉታዊ አመለካከታቸው ጥልቀት የቱን ያህል እንደሆነ የሚያመለክት ነው። *የፍትሕ..ወዴት ነው?* ከኢሳ5፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

3፥1 *መልእክተኛዬን፤* ይህ ቃል በዕብራይስጡ፣ “ማላኪ” ተብሎ የሚጠራ ሲሆን ይህም ነቢይ ወይም ካህን የሚጠራበት ስም ነው። (ሐጌ1፥13እና ማብ ይመ)። ትንቢቱ በመጥምቁ ዮሐንስ መምጣት ተፈጽሞአል (ማቴ11፥10፤ማር1፥2፤ ሉቃ1፥76 ይመ) *መንገድ እንዲያዘጋጅ፤* ጌታ የሚመጣው፣ ለማጥራትና (ቍ3)፤ ለመፍረድ (ቍ5)፤ ነው፤ ነገር ግን ከምሕረቱ የተነሣ ሕዝቡን ለማዘጋጀት ሲል አስቀድሞ መልእክተኛውን ይልካል (4፥5-6እና ማብ እንዲሁም ኢሳ40፥3እና ማብ ይመ)። *የምትፈልጉት ጌታ...ደስ የምትሰኙበትም...ይመጣል፤* ሐጌ 2፥7 እና ማብ ይመ ። *የቃል ኪዳኑ መልእክተኛ፤* መሲሑ እግዚአብሔርን በመወከል፣ ቃል ኪዳኑን ይመሠርታል፣ ያጸናልም (የኢሳ 42፥6 ማብ ይመ)።

3፥2 *የሚመጣበትን ቀን፤* የጌታን ቀን ማለት ነው።(4፥1 ይመ። እንዲሁም የኢሳ2፥11፡17፡20 ማብ ይመ)። ሚልክያስ እግዚአብሔር በዓለም ታሪክ ውስጥ የሚያከናውነውን ሥራ፣ በተለይም በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የተገለጸውን ትንቢት ለመፈጸም ጌታ እንደሚመጣ በይፋ ተናግሮአል፤ ይህም በመሲሑ መምጣት ተፈጽሞአል። *መቆም የሚችል ማነው?* የጌታን መምጣት የሚናፍቁ ሰዎች ንጹሕ ልብና የጠራ እጅ ሊኖራቸው እንደሚገባ ማወቅ ይኖርባቸዋል (ከመዝ24፥3-4፣ኢሳ33፥14-15 ጋር ያነጻጽሩ)። *እንደ አንጥረኛ እሳት፤* ኢሳ1፥25፤ ዘካ13፥8-9 እና ማብ ይመ። እንደ ልብስ አጣቢ ሳሙና፤ ኢሳ 7፥23 እና ማብ ይመ። ነጭ ልብስ ንጽሕናን ያመለክታል ከማር 9፥3፤ ራእይ 3፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥3 *ሌዋውያንንም... አንጽቶ፤* በ1፥6-2፥2 ላይ የተገሠጹት፣ የጌታ “መልእክተኞች” እንዲሁም በመሠዊያው ላይ የሚያገለግሉት፣ ከኀጢአታቸውና ታማኝ ካለመሆናቸው ሊነጹ ይገባቸዋል።

3፥4 *ደስ የሚያሰኝ፤* 1፥8 እና ማብ ይመ። እንዳለፉት ቀናትና፤ ምናልባት የሙሴንና የፊንሐስን ዘመን ማለት ይሆናል (የ2፥5 ማብ ይመ)።

3፥5፤ እግዚአብሔር ሲመጣ፣ ጌታ ሌዋውያንን ያነጻል (ቍ3-4) በሕዝቡም ላይ ይፈርዳል። *በመተተኞች፤* በጥንቱ ቅርብ ምሥራቅ አገሮች የተለመደ ነገር ነው (ዘፀ7፥11፤ዘዳ18፥10 ይመ)።

3፥6 አልለወጥም፤ ያዕ 1፥17 ይመ። በሚልክያስ ዘመን የነበሩት ብዙዎች እንደሚያስቡት ሳይሆን፣እግዚአብሔር ምን ጊዜም ለገባው ኪዳን በታማኝነት ጸንቶ የሚገኝ አምላክ ነው። የጠፋችሁ አይደላችሁም፤ ንጽጽሩ ከኤዶም ጋር (1፥3-5) እንዲሁም በእስራኤላውያን ታሪክ ውስጥ እንደሚታየው በታማኝነት ጸንቶ ካለመገኘት ጋር ነው።

3፥7 *ተመለሱ፤ እኔም...እመለሳለሁ፤* ጌታ የሚመጣው እስ

ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት።

“እናንተ ግን፣ የምንመለሰው እንዴት ነው ትላላችሁ?”

[8]“ሰው እግዚአብሔርን ይሰርቃልን?” እናንተ ግን ትሰርቁኛላችሁ።

“እናንተ ግን፣ ‘እንዴት እንሰርቅሃለን?’ ትላላችሁ።

“በሥራትና መባ ትሰርቁኛላችሁ፤ እናንተም፣ መላው ሕዝባችሁም ስለምትሰርቁኝ የተረገማችሁ ናችሁ። [10]በቤቴ መብል እንዲኖር፣ እኔንም በዚህ እንድትፈትኑኝ ዐሥራቱን ሁሉ ወደ ጐተራ አስገቡ፤” ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት፤ “የሰማይን መስኮት የማልከፍትላችሁ፣ የተትረፈረፈ በረከትንም ማስቀመጫ እስኪታጣ ድረስ የማላፈስላችሁ ከሆነ ተመልከቱ። [11]ስለ እናንተ ተባዩን እገሥጸለሁ፤ አዝመራችሁን አይበላም፤ ዕርሻ ላይ ያለ የወይን ተክላችሁም ፍሬ አልባ አይሆንም” ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት። [12]“ከዚያም በኋላ የተድላ ምድር ስለምትሆኑ ሕዝቦች ሁሉ የተባረከ ሕዝብ ብለው ይጠሯችኋል” ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት።

[13]“በእኔ ላይ የድፍረት ቃል ተናግራችኋል” ይላል *እግዚአብሔር*።

“እናንተ ግን፣ ‘በአንተ ላይ የተናገርነው ምንድን ነው?’ ትላላችሁ።

[14]“እንዲህም ብላችኋል፤ ‘*እግዚአብሔርን* ማገልገል ከንቱ ነው፤ እርሱ የሚፈልገውን ሁሉ በማድረግና *በእግዚአብሔር* ጸባኦት ፊት ሐዘንተኞች ሆነን በመመላለስ ምን ተጠቀምን? [15]አሁን ግን ትዕቢተኞችን ቡሩካን እንላቸዋለን፤ ክፉ አድራጊዎች ይበለጽጋሉ፤ እግዚአብሔርን የሚፈታተኑትም ያመልጣሉ።’”

[16]በዚያን ጊዜ *እግዚአብሔርን* የሚፈሩ ሰዎች እርስ በርሳቸው ተነጋገሩ፤ *እግዚአብሔር* አዳመጠ፤ ሰማቸውም፤ *እግዚአብሔርን* ለሚፈሩና ስሙን ለሚያከብሩ በእርሱ ፊት የመታሰቢያ መጽሐፍ ተጻፈ።

[17]“እኔ በምሠራበት ቀን እነርሱ የግል ገንዘቤ″ ይሆናሉ” ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት፤ “አባት የሚያገለግለውን ልጁን እንደሚታደግ ሁሉ እኔም እታደጋቸዋለሁ። [18]በዚያን ጊዜም እንደ ገና በጻድቁና በኀጢአተኛው መካከል፣ *እግዚአብሔርን* በሚያገለግለውና በማያገለግለው መካከል ያለውን ልዩነት ታያላችሁ።

## *የእግዚአብሔር ቀን*

**4** “እነሆ፤ እንደ ምድጃ እሳት የሚነድ ቀን ይመጣል፤ ትዕቢተኞች ሁሉና ክፉ አድራጊዎች በሙሉ ገለባ ይሆናሉ፤ ያ የሚመጣው ቀንም ያቃጥላቸዋል” ይላል *እግዚአብሔር* ጸባኦት። “ሥርም ሆነ ቅርንጫፍ አያስቀርላቸውም። [2]ስሜን ለምትፈሩ ለእናንተ ግን የጽድቅ ፀሐይ በክንፎቿ ፈውስ ይዛ ትወጣለች፤ እናንተም ከጋጥ እንደ ተለቀቀ እንቦሳ እየቦረቃችሁ ትወጣላችሁ። [3]እኔ በምሠራበት ቀን ክፉዎችን ትረግጣላችሁ፤ ከእግ

3፥7 ዘዐ32፥8፤ ኢሳ44፥22፤ ኤር7፥26፤ ሕዝ18፥32፤ ዘካ1፥3፤ሚል1፥2፤ ሐሥ7፥51፤ያዕ4፥8
3፥8 ዘኍ13፥10-12፤ 18፥21፤ዘሌ27፥30፤ ዘካ5፥3፤ሉቃ18፥12
3፥9 ዘዳ11፥26፤ 28፥15-68፣ዘካ5፥3
3፥10 ዘዐ22፥29፤ ዘሌ25፥21፤2ነገ7፥2፤ ነህ13፥12፤ ኢሳ44፥3፤ኢል2፥14፡ 24፤2ቆሮ9፥8-11
3፥11 ዘዳ28፥39፤ ዘዐ10፥15፤ ኢሳ61፥9፤62፥4፤ ሕዝ20፥6
3፥12 ዘዳ28፥3-12፤ 2ዜና31፥10፤ ኢሳ61፥9፤62፥4፤ ሕዝ20፥6
3፥13 ሚል1፥2፤ 2፥17
3፥14 ኢሱ22፥5፤ መዝ73፥13፤100፥2
3፥15 ኢዮ21፥7፤ መዝ14፥1፤119፥21፤ ኤር7፥10
3፥16 ዘዐ32፥32፤ ዘዳ28፥58፤31፥12፤ መዝ33፥18፤34፥15፤ 56፥8፤87፥6፤ ምሳ1፥7፤ሉቃ10፥20፤ ራእ11፥18
3፥17 ዘዐ8፥22፤ ዘዳ7፥6፤ነህ13፥22፤ መዝ103፥13፤ ኢሳ26፥20፤43፥21፤ ሉቃ15፥1-32፤ ሮሜ 8፥14፥21፤ ሉቃ15፥1-32፤ ሮሜ 8፥14፡32፤ ቲቶ2፥14
3፥18 ዘፍ18፥25፤ ዘዳ32፥4፤ማቴ25፥32-33፡41 4፥1 2ነገ10፥11፤ ኢሳ1፥31፤ 2፥2፤5፥24፤31፥9፤ሕዝ17፥8፤ዳን7፥13፤ኢ2፥31፤ ናሆ1፥10፤ማቴ3፥10፤11፥14፤ሐሥ2፥20 4፥2 ዘዳ28፥58፤ ዜና7፥14፤ መዝ61፥5፤111፥9፤118፥27፤ኢሳ9፥2፤ 30፥26፤ 35፡35፥6፤45፥8፤ ማቴ4፥23፤ ሉቃ1፥78፤ ኤፌ5፥14፤ ራእ14፥1፤22፥2
4፥3 ኢዮ40፥12፤ መዝ40-42፤ ሕዝ28፥18

″17 ወይም ሁሉን ቻይ፤ “*እኔ በምሠራበት ጊዜ ንብረቴ ይሆናሉ*”

ራኤልን ለመበዝበዝ እስከ ሆነ ድረስ፤ እርሷም ንስሓ መግባት ይገባታል።

3፥9 *የተረገማችሁ፤* 2፥2 እና ማብ ይመ።

3፥10 *ወደ ጐተራ፤* የቤተ መቅደስ ዕቃዎች የሚቀመጡባቸው የተለያዩ ክፍሎች (1ነገ7፥51፤2ዜና31፥11-12፤ ነህ13፥12 ይመ) *የሰማይን መስኮት፤* አባባሉ በሌላ ቦታ የሚያመለክተው የምግብን መትረፍረፍ ነው (2ነገ 7፥2፡19፤ መዝ 78፥23-24 ይመ)። በረከትንም የማላፈስላችሁ፤ ተስፋ የተሰጠበት የቃል ኪዳን በረከት (ዘዳ 28፥12 ይመ)፤ ከኢሳ 44፥3 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥11 *ተባዩን...ፍሬ አልባ፤* የሚያስፈራውን የቃል ኪዳን ርግማን የሚያሳስብ ምሳሌ ነው። (ዘዳ 28፥39-40)።

3፥12 *የተባረከ ሕዝብ ብለው ይጠሯችኋል፤* ይህ የሚሆነው ለአብርሃም የተሰጠው ተስፋ ሲፈጸም ነው። (ዘፍ 12፥2-3 ይመ፤) እንዲሁም ኢሳ 61፥9 እና ማብ ይመ)።

3፥14 *እግዚአብሔርን ማገልገል ከንቱ ነው፤* ይህን ያሉበትም ምክንያት እነርሱ የናፈቁት መቤዠት ገና ስላልተፈጸመ ነው። *ሐዘንተኞች ሆነን፤* ማቅ በመልበስና፤ ዐመድ በመነስነስ ማለት ነው።

3፥15 *ትዕቢተኞችን፤* እግዚአብሔርን የሚፈታተኑ ክፉ አድራጊዎችን ማለት ነው፤ (የመዝ10፥11 ማብ ይመ)። *ቡሩካን፤ እግዚአብሔርን የሚፈሩ ሰዎች፣* “የተረገሙ” ብለው የሚጠሯቸውን አይሁድ ግን ባለማመናቸው ምክንያት “ቡሩካን” ብለው ይጠሯቸዋል፤ (መዝ 119፥21 ይመ)፤ አይሁድ ንስሓ ቢገቡ ኖሮ “ቡሩካን” የሚባሉት ሌሎች ሳይሆኑ እነርሱ ራሳቸው ነበሩ (ቍ12)። *ክፉ አድራጊዎች ይበለጽጋሉ...ያመልጣሉ፤* መዝ73፥3፤ 9-12 ላይ መዝሙረኛው የክፉ ሰዎች መበልጸግ እንዴት እንቆቅልሽ እንደሆነበት ይመልከቱ።

3፥16 *እግዚአብሔርን የሚፈሩ፤* ለጥርጣሬና ለአሉታዊ አስተሳሰብ ቦታ ያልሰጡ ማለት ነው። *እርስ በርሳቸው ተነጋገሩ፤* በእግዚአብሔር ላይ ማጕረምረም በነገሠበት በዚያ ዘመን ፈሪሀ እግዚአብሔር የነበራቸው ሰዎች ከቍ14-15)። እርስ በርስ መበረታታት እንደሚያስፈልጋቸው ተገንዝበዋል ማለት ነው። *የመታሰቢያ መጽሐፍ፤* ምድራዊ ገዦች መልካም የሆነን ሥራ መዝግበው እንደሚይዙት ማለት ነው። አስ6፥1-3፤ኢሳ4፥3፤ ዳን7፥10፤ 12፥1 ይመ)። *ስሙን ለሚያከብሩ፤* ከካህናቱ ጋር(1፥2) እና በሕዝቡ መካከል ካሉ አንዳንድ ሰዎች (ቍ14-15፤2፥17) ጋር ያነጻጽሩ።

3፥17 *ገንዘቤ፤* የዘፀ19፥5 ማብ ይመ። *እታደጋቸዋለሁ፤* በፍርድ ቀን ማለት ነው (4፥1-2 ይመ)። *የሚያገለግለውን፤* ከ1፥6 ጋር ያነጻጽሩ።

3፥18 እንደ ገና...ታያላችሁ፤ ከአሉታዊ አመለካከታቸው የተነሣ አሁን ባያዩትም ማለት ነው 2፥17እና ማብ ይመ።

4፥1 *እንደ ምድጃ እሳት፤* 3፥2-3፤ኢሳ1፥31፤ 66፥15-16 እና ማብ ይመ። *ቀን፤* የእግዚአብሔር ቀን ማለት ነው(ቍ5፤ 3፥2እና ማብ ይመ)። *ትዕቢተኞች፤* 3፥15 እና ማብ ይመ። *ገለባ...ያቃጥላቸዋል።* ኢሳ 47፥14 እና የክርስቶስን ሥራ በተመለከተ የመጥምቁ ዮሐንስን ትንቢት ማቴ 3፥12 ላይ ይመ። *ሥርም ሆነ ቅርንጫፍ፤* ከቃጠሎው የሚተርፍ አንዳች ነገር የለም (ሕዝ 17፥8-9 ይመ)።

4፥2 *የጽድቅ ፀሐይ፤* በኢሳ 60፥1፡19 ላይ እንዲሁም (ማብ ይመ)። እግዚአብሔርና ክብሩ ከፀሓይ ጋራ ተነጻጽረዋል። ክርስቶስ “ከላይ የመጣ ብርሃን” ነው። (ሉቃ 1፥78-79፤ እንዲሁም ኢሳ 9፥2 እና ማብ ይመ)። *የጽድቅ...ፈውስ፤* የድነትንና የተሐድሶ ተስፋ እንዳለ ያሳያል ኢሳ 45፥8፤46፥13፤ 53፥5፤ ኤር 30፥17 እና ማብ ይመ)። *በክንፎቿ፤* የፀሓይ ጸዳል (ከመዝ 139፥9ጋር ያነጻጽሩ)። ከታሰረበት ሲፈታ *እንደ ተለቀቀ እምቦሳ፤* የታሰረ እምቦሳ ከታሰረበት ሲፈታና ነጻ ሲሆን ሚዳው አይበቃውም፤ ፈንጭቶም አይደክመውም።

ራችሁ ጫማ በታች ዐመድ ይሆናሉ" ይላል እግዚአብሔር ጸባኦት።

[4]"ለእስራኤል ሁሉ ሕጎችና ሥርዐቶች ይሆኑ ዘንድ፣ ለአገልጋዬ ለሙሴ በኮሬብ የሰ ጠሁትን ሕግ አስቡ።

[5]"እነሆ፤ ታላቁና የሚያስፈራው የእግዚአ ብሔር ቀን ከመምጣቱ በፊት፣ ነቢዩ ኤል ያስን እልክላችኋለሁ። [6]መጥቼ ምድርን በርግማን እንዳላጠፋ፣ እርሱ የአባቶችን ልብ ወደ ልጆች፣ የልጆችንም ልብ ወደ አባቶች ይመልሳል።"

4፥4 ዘፀ3፥1፤20፥11፤ ዘዳ28፥61፤መዝ147፥19፤ ማቴ5፥17፤7፥12፤ ሮሜ2፥13፤4፥15፤ ገላ3፥24
4፥5 1ነገ17፥1፤ ኢል2፥31፤ ማቴ11፥14፤ 16፥14
4፥6 ዘዳ11፥26፤ 13፥15፤ ኢሱ6፥17፤23፥15፤ኢሳ11፥4፤ ዘካ5፥3ሉቃ1፥17፤ ራእ19፥15

4፥3 *ክፉዎችን...ትረግጣላችሁ፤* አንድ ሰው የወይን መጭ መቂያን እንደሚረግጥ ማለት ነው (ኢሳ63፥2-3እና ማብ ይመ)።

4፥4 *ሕግ አስቡ፤* የጌታን መምጣት በትዕግሥት መጠበቅ ላቃታቸው ሰዎች የተሰጠ የመጨረሻ የመንፈስ ማበረታቻ ነው። *ለአገልጋዬ፤* ዘፀ14፥31፤ ዘዳ34፥5፤ መሳ2፥8፤ መዝ18 ርእስ፤ ኢሳ 20፥3፤41፥8-9፤42፥1 እና ማብ ይመ። *በኮሬብ፤* የሲና ተራራ ነው (ከዘፀ3፥1 ጋር ያነጻጽሩ)።

4፥5፤ 3፥1 እና ማብ ይመ። *ኤልያስን፤* ኤልያስ የፍርድና የመዋጀት አገልግሎት ካገለገለው ከኤልሳዕ በፊት እንደ መጣ ሁሉ፣ ኤልያስም የእግዚአብሔርን ሕዝብ ለጌታ መምጣት ለማዘ ጋጀት ይላካል። መጥምቁ ዮሐንስም ያገለገለው "በኤልያስ መንፈስና ኀይል" ነው (ሉቃ1፥17፤ማቴ11፥13-14፤17፥12-13፤ማር 9፥11-13 ይመ)። አንዳንድ ሰዎች በራእ 11፥3 ላይ ከተገለጹት ከሁ ለቱ ምስክሮች አንዱ ኤልያስ ነው ይላሉ። *ታላቁና የሚያስፈራው ... ቀን፤* ቀ 1፤3፥2 እና ማብ፤ ኢዮ 2፥11፡31 ይመ።

4፥6 *ልብ...ይመልሳል፤* ከዘፍ 18፥19፤ ዘዳ 7፥9-11 ጋር ያነጻጽሩ። በሉቃ 1፥17 መሠረት በመጥምቁ ዮሐንስ አገልግሎት ይህ ተፈጽሞአል። *በርግማን፤* ፍጹም ጥፋትን የሚያመለክት ነው። እግዚአብሔር ኤዶምን እንደ ቀጣት ሁሉ እስራኤልም ንስሓ የማትገባ ከሆነ፣ እርሷንም ይቀጣታል (ኢሳ 34፥5፤ ከሚል 1፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ)።

## ከሚልክያስ እስከ ክርስቶስ

### የፋርስ ዘመን 450-330 ዓ.ቅ.ክ

ከነህምያ በኋላ ለ200 ዓመታት የፋርስ መንግሥት ይሁዳን በቀጥጥሩ ሥር አድርጎ ቢቀይም አይሁዶች ግን ሃይማኖታዊ ሥርዐቶቻቸውን ያለ ችግር ያካሂዱ ነበር። በዚህ ጊዜ የይሁዳ ምድር ለአይሁድ መንግሥት ኀላፊነት በነበረው በሊቀ ካህናት ይተዳደር ነበር።

### የታላቁ እስክንድር መንግሥት

### የግሪክ ዘመን 330-166 ዓ.ቅ.ክ

በ33 ዓ.ቅ.ክ በመቄዶንያ ሰፍሮ የነበረው የፋርስ ሠራዊት በታላቁ እስክንድር ተሸነፈ። እርሱም ዓለምን አንድ ሊያደርግ የሚችለው የግሪክ ጠንካራ ባሕል እንደሆነ አመነ። አይሁዶች ሃይማኖታዊ ሥርዐታቸውን እንዲፈጽሙ፤ በሰባተኛው ዓመት ከግብር ነጻ እንዲሆኑ፤ የእስክንድርያ ከተማን ከሠራ በኋላ አይሁዶች እዚያ እንዲኖሩ በግሪክ ግዛት ሥር ካሉ ሕዝቦች ጋር እኩል መብት ሰጣቸው። የግሪክ ብዙ አገሮች መያዝ የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ወደ ግሪክ ቋንቋ እንዲተረጎሙ መንገድ ከፈተ (የሰብዓ ሊቃናት ትርጉም በ250 ዓ.ቅ.ክ ተተረጎመ)

የግብፁ በጥሉሜስ መንግሥት

የሶሪያ መንግሥት ሴሉ ሲድ

### የአስሞኒያን ዘመን 166-63 ዓ.ቅ.ክ

ይህ ታሪካዊ ዘመን ሲጀመር አይሁዳውያን በከፋ ሁኔታ ይጨነቁ ነበር። የበጥሉሜስ ገዢዎች የአምልኮ ሥርዐታቸውን እንዲፈጽሙ ፈቅደው ነበር፤ የሴሉሲድ ገዢዎች ግን የግሪክን ባሕል በግድ እንዲከተሉ ያደርጓቸው፤ ቅዱሳት መጻሕፍትን በማቃጠል የሕግ ሜና ያበዛ ባቸው ነበር። የተጨቆኑት አይሁዶች በይሁዳ መቃብያን በመመራት በመቃ።

የአስሞኒያን ሥርወ መንግሥት

### የሮም ዘመን 63 ዓ.ቅ.ክ

በ63 ዓ.ቅ.ክ የሮም ጀኔራል ፖምፒ ኢየሩሳሌምን ያዘ፤ የፍልስጥኤም አውራጃዎችም ለሮም ግብር ሆኑ። በአካባቢው የነበረው መንግሥት አንዳንዱን ክፍል ለልዑላን ሌላውን/ ደግሞ ለአገረ ገዢነት በተሾሙ ባለ ሥልጣናት ይተዳደር ነበር። ክርስቶስ በተወለደበት ዘመን ታላቁ ሄሮድስ በፍልስጥኤም ምድር ሁሉ ላይ ይገዛ ነበር።

ታላቁ ሄሮድስ በሮማ ሥር ሆኖ እንደ ንጉሥ ይገዛ ነበር

410 400 390 380 370 360 350 340 330 320 310 300 290 280 270 260 250 240 230 220 210 200 190 180 170 160 150 140 130 120 110 100 90 80 70 60 50 40 30 20 10 — 10 20 30

- 334 - 323 ታላቁ እስክንድር የምሥራቁን ዓለም ያዘ
- 330 - 328 ታላቁ እስክንድር በሥልጣን የቆየበት
- 320 ቀዳማዊ በጥሊሞስ ኢየሩሳሌምን ያዘ
- 311 ሴሉኩስ ባቢሎንን ያዘ፤ የሴሉሲድ ሥርወ መንግሥት ጀመረ
- 226 የሶሪያው አንጥዮኩስ ሳልሳዊ (ታላቁ) ፍልስጥኤምን ያዘ
- 223 - 187 አንጥዮኩስ የሶሪያ ንጉር ሆነ
- 198 አንጥዮኩስ ግብፅን በማሸነፍ ፍልስጥኤምን ያዘ
- 175 – 164 አንጥዮኩስ አራተኛ ኤጲፋኔስ የሶሪያ ንጉር ሆነ፤ ይሁዲነት ተከለከለ።
- 167 ማትያስና ልጆቹ በአንጥያኮስ ላይ ዐመፁ፤ የመቃብያን ዐመፅ ጀመረ።
- 166 160 ሃይሁዳ መቃብያን መሪነት
- 160 - 143 ዮናታን ሊቀ ካህናት ሆነ
- 142 የኢየሩሳሌም ??????????
- 142 - 134 ስምኦን ሊቀ ካህናት ሆነ፤ የአስሞንያን ሥርወ መንግሥትን መሠረተ
- 134 - 104 ዮሐንስ ሒርካኑስ ነጻ የአይሁድ ግዛትን አስፋፋ
- 103 የአርስጦቡሉስ ግዛት
- 102 - 76 የእስክንድርያ ኢያኔዎስ ግዛት
- 75 - 67 የሰሎሜ እስክንድርያ እና ዳግማዊ ሂርቃኑስ እንደ ሊቀ ካህናት ሆኖ በጋራ የነው የገዙት
- 66 - 63 በዳግማዊ አርስጦቡሊስና በዳግማዊ ሂርቃኑስ መካከል የተደረገ ጦርነት
- 63 ፖምፒ ፍልስጥኤምን ወረረ፤ የሮም ግዛት ጀመረ
- 63-40 ዳግማዊ ሂርቃኑስ በሮም ሥር ሆኖ መግዛት ጀመረ
- 40-37 ጳርጢያኖች ኢየሩሳሌምን ያዙ
- 37 ኢየሩሳሌም ለስድስት ወር ተከበበች
- 32 ሄሮድስ ተሸነፈ
- 19 የሄሮድስ ቤተ መቅደስ ሥራ ተጀመረ
- 16 ሄሮድስ አግሪጳን ጎበኘ
- 4 ሄሮድስ ሞተ፤ አርኬሌዎስ ተተካ

# በሁለቱ ኪዳናት መካከል የነበረው ዘመን

በሁለቱ ኪዳናት መካከል የነበረው ዘመን፣ ውስጥ ውስጡን ሲብላላ የቈየና ለውጥ የተካሄደበት ዘመን ነው። ይህ ዘመን በመካከለኛው ምሥራቅ አካባቢ ለ3000 ዓመት ያህል ተንሰራፍቶ የቈየው ባሕል እየጠፋ፣ የኀይል ሚዛን በአዲስ መልክ እየተዋቀረ የመጣበት ወቅት ነው።

በመጽሐፍ ቅዱስ ታሪክ፣ ነህምያ በነበረበትና ክርስቶስ በተወለደበት ዘመን መካከል ያለው (በግምት የ400 ዓመት) ጊዜ፣ በኪዳናት መካከል ያለው ዘመን (432-5 ዓ.ቅ.ክ) በመባል ይታወቃል። አንዳንድ ጊዜ፣ "የዝምታው ዘመን" ተብሎ ይጠራል። ነገር ግን የዚህ ዘመን ሁነቶች፣ ሥነ ጽሑፎችና ማኅበራዊ ግንኙነቶች የዘመነ አዲስን ዓለም በአጅጉ ቀርጸውታል።

## ታሪክ

ከባቢሎናውያን ምርኮ የተነሣ እስራኤል ራሷን የቻለች አገር መሆኗ ቀርቶ፣ የታላላቆቹ ዐፄ ግዛቶች ትንሽ ግዛት ሆነች። በኪዳናት መካከል ያለውን ዘመን አስመልክቶ በቀደምት የታሪክ ምንጭነት የሚጠቀሰው አይሁዳዊው ታሪክ ጸሐፊ ዮሴፍ ወልደ ኮሪዮን (ጆሴፈስ) ስለ ፋርሶች የጻፈው አንዳች ነገር ባለመኖሩ በዚያ አቅጣጫ የሚታወቅ ብዙ ነገር የለም።

ታላቁ እስክንድር ፓለስቲናን (332 ዓ.ቅ.ክ)የግዛቱ አካል ከማድረጉ የተነሣ እስራኤል አዲስና ለውጥ የሆነ ጥቃት ይደርስባት ጀመረ። እስክንድር ዓለምን በግሪክ ቋንቋና ባሕል ሥር የማድረግ ዐላማ ያለው ሰው ነበር። 'ሔለናይዜሽን' የተባለው ይህ አስተሳሰብ (ፖሊሲ) እርሱን በተከተሉት ሰዎችም ዘንድ ተቀባይነት ነበረው። ፖሊሲው በተለይ በአይሁዳውያን ላይ ታላቅ ተጽዕኖ ማስከተሉ አልቀረም።

እስክንድር በ323 ዓ.ቅ.ክ ሲሞት ድል አድርጎ የያዛቸው የዐፄ ግዛቶች፣ ለጦር ጀኔራሎቹ ተከፋፈሉ። ከእነዚህም መካከል ሁለቱ ጀኔራሎች ሥርወ መንግሥት መሠረቱ፤ እነዚህም በግብፅ የነገሠው በጥሊሞስና በሶርያና በመስጴጦምያ የነገሠው ሴሉዊሲድ ነበሩ። ይህም ፓለስቲናን ከአንድ ምእተ ዓመት በላይ ለመቈጣጠር ትልቅ ሚና ተጫውቶአል።

የበጥሊሞስ አመራር ለአይሁድ ሃይማኖታዊ ቅናት ስፍራ የሚሰጥ ነበር፤ ነገር ግን በ198 ዓ.ቅ.ክ. ላይ፣ ሴሉዊሲድ አካባቢውን በመቈጣጠር በአይሁድ ታሪክ ውስጥ እጅግ በጣም ከሚታወቁት የጀግንነት ዘመናት መካከል ለአንዱ ጥርጊያ መንገድ ከፈተ።

የመጀመሪያው የሴሉዊሲድ አገዛዝ ዘመን፤ እንደ በጥሊሞስ ሰላም የሰፈነበት ነበር፤ ከ175-164 ዓ.ቅ.ክ ነግሦ የነበረው አራተኛው አንጢያኮስ ኢጲፋኔዎስ ("የተገለጠ እግዚአብሔር") ግን በመፍረክረክ ላይ ያለውን የሔሌናይዜሽን ፖሊሲ እንደ መፍትሔ አድርጎ ተጠቀመበት። የአይሁድ ነገሥታት ቤተ ሰቦች፣ የግሪካውያኑን ልማድ ቀድሞውኑ ገንዘባቸው ቢያደርጉትም፣ በአብዛኞቹ አይሁድ ዘንድ ግን ሔሌናይዜሽን ቍጣን ቀስቅሶአል።

የአንጢያኮስ አመራር ያነጣጠረው የአይሁድን ሃይማኖት በማጥፋት ላይ ነበር። ስለዚህም መሠረታዊ የሚባሉ የአይሁድ ሃይማኖታዊ ሥርዐቶች እንዳይከናወኑ በጥብቅ ከለከለ፤ አምስቱን የሙሴ መጻሕፍት ቅጆች ሁሉ የማጥፋት ሙከራ አደረገ፤ እንዲሁም ሱስ ለሚባለው የሚመለክ ጣዖት መሥዋዕት እንዲቀርብ አዘዘ፤ በተለይም የዚህን ጣዖት ምስል ማቆሙና በኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ በሣማ መሠዋቱ ታላቅ ቍጣን ቀስቀሰ።

በአንጢያኮስ ላይ የተካሄደው ተቃውሞ የተመራው፣ በአንድ ትንሽ መንደር በሚኖረውና ከካህናት ቤተ ሰብ በተወለደው በሽማግሌው ማታቲያስና በአምስት ልጆቹ ነበር። እነርሱም ይሁዳ (መቃቢዮስ)፣ ዮናታን፣ስምዖን፣ዮሐንስና ኤሊዓዘር ይባላሉ። ማታቲያስ ሞዲን በተባለችው የእርሱ መኖሪያ መንደር የተተከለውን የጣዖት መሠዊያ አፈረሰ፤ ከአንጢያኮስ ዘንድ በምስጢር የተላከውንም መልእክተኛ ገደለ። ይህም 24 ዓመት ያዋጋውን (166-142 ዓ.ቅ.ክ) የመቃብያንን ሀመፅ ቀስቀሰ። ሮማውያን በ63 ዓ.ቅ.ክ አካባቢውን እስከ ተቈጣጠሩበት ጊዜ ድረስም፣ ይሁዳ በማንም ላይ ጥገኛ ሳትሆን መቈየት እንድትችል መንገድ ከፈተ።

የማታቲያስ ቤተ ሰቦች ድል በታላቅ ገድል የተገኘ ቢሆንም እንኳ፣ ከመጨረሻ ልጁ ከስምዖን ሞት በኋላ መሥርተውት የነበረው የሐስሞናውያን ሥርወ መንግሥት ቀስ በቀስ ወደ ንጉሣዊ አስተዳደር ተቀየረ። የሔሌናይዜሽንን አስተዳደር ከሴሉዊሲድ አስተዳደር ለይቶ መመልከት አንዳንዴ አስቸጋሪ ነው። ከስምዖን ልጅ ከዮሐንስ አርቃኔዎስ ንግሥና በኋላ መቃብያንን ይደግፉ የነበሩት ርቱዓን አይሁድ ተቀባይነት እያጡ መጡ። ከጥቂቶቹ በስተቀር ሐስሞናውያን አይሁድ የሔሌናይዜሽን ደጋፊዎች ሆኑ። ፈሪሳውያንም በታላቁ ጃኒ

ዎስ (102-76 ዓ.ቅ.ክ) መስደድ ጀመሩ::

በ63ዓ.ቅ.ክ ላይ የሐስሞናውያን ሥርወ መንግሥት አከተመ:: በመስፋፋት ላይ ያለው የሮማውያን የዐፄ ግዛት በሁለቱ የጃኔዎስ ልጆች፣ ማለትም በዳግማዊ አርስጦቡሎስና በዳግማዊ ሒርካኔዎስ የሥልጣን ሽኩቻ መካከል ጣልቃ ገባ:: የምሥራቁን ክፍለ ዓለም የገዛው ፓምፒ የተባለው የጦር ጀነራል፣ ከሦስት ወር ከበባ በኋላ በቤተ መቅደስ በአገልግሎት ላይ የነበሩትን ካህናት በመጨፍጨፍ ወደ ቅድስተ ቅዱሳኑ ገባ:: ይህ በሮማውያን አስተዳደር መጀመሪያ ላይ የተፈጸመው አሰጸያፊና አስቃቂ ድርጊት በአይሁድ ዘንድ የሚረሳና ይቅር የሚባል ሊሆን አልቻለም::

ሥነ ጽሑፍ

በእነዚህ ደስ በማያሰኙ፣ የፍጭቄና የውስጥ ችግር በነገሠባቸው ዓመታት፣ የአይሁድ ሕዝብ ተጽፈው የተቀመጡና የዘመኑን ሁኔታ የሚያወሡ አዋጋቢ ጽሑፎችን ትተው ዐልፈዋል:: ከነዚህም ውስጥ እጅግ ከፍተኛ የሆነ ጠቀሜታ ያላቸው ሦስቱ ሥራዎች የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም፣ አዋልድ መጻሕፍትና የሙት ባሕር ጥቅልሎች ናቸው::

የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም፤

የአይሁድ አፈ ታሪክ እንደሚያስረዳው፣ በ250ዓ.ቅ.ክ ገዳማ በበጥሊሞስ ፊላደልፈስ ኀላፊነት፣ 72 ሊቃውንት በአሌክሳንደርያ አቅራቢያ በምትገኘው በፋሮስ ደሴት ላይ፣በ72 ቀናት ውስጥ የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትን ወደ ግሪክ (ጽርእ) ተረጐሙ:: ከዚህ ትውፊት የተነሣ መጽሐፉ ሴፕቱዋጀንት፣ "የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም" ተብሎ ተጠራ:: ስሙን በምኅጻረ ቃል ለመጻፍ የሮማውያንን 70 ቍጥር (LXX) የምንጠቀምበት ለዚህ ነው::

ከትውፊቱም በተጨማሪ አምስቱ የሙሴ መጻሕፍት፣ በእስክንድርያ ይኖሩ ለነበሩት የግሪክ ቋንቋ ተናጋሪ አይሁድ ሲባል ወደ ግሪክ ቋንቋ የተተረጐሙት 250ዓ.ቅ.ክ ላይ ነው የሚል ግምት አለ:: የተቀሩት የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትና አዋልድ መጻሕፍት፣ በሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ውስጥ የተጨመሩት የክርስትና ሃይማኖት ከመጀመሩ በፊት ነው፤ ነገር ግን የተጻፉበት ዘመን በትክክል አይታወቅም::

የሰብዓ ሊቃናት ትርጕም ከፓለስቲና ወጭ፣ እንደ እስክንድርያ ባሉ አካባቢዎች ለሚኖሩትና የአይሁድን ቋንቋ ለማያናገሩት አይሁድ መጽሐፍ ሆነ:: ይህ ትርጕም ያመጣው አሉታዊ ተጽዕኖ ምን ያህል እንደ ሆነ በትክክል ማወቅ ባይቻልም እንኳ፣ የአባቶቻቸውን ቋንቋ መናገር ለማይችሉት አይሁድና የግሪክ ቋንቋ ለሚናገረው ዓለም ተዘጋጅቶ የቀረበ የብሉይ ኪዳን ቅጅ ነበር:: በኋላም መጽሐፉ የጥንቷ ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ሆነ::

አዋልድ መጻሕፍት

አዋልድ ስሚለው የግሪኩ አቻ ቃል "አፖክሪፋ" የሚለው ሲሆን ትርጕሙም፣ "የተደበቀ" ማለት ነው:: አዋልድ መጻሕፍት በመባል የሚታወቁት በሁለቱ ኪዳናት መካከል የተጻፉት መጻሕፍት ናቸው:: እነዚህ መጻሕፍት በሮማና በምሥራቅ አብያተ ክርስቲያናት ዘንድ፣ እንደ እግዚአብሔር ሥልጣናዊ ቃል የመታየታቸው ጕዳይ ውስብስብ የሆነ ታሪካዊ ዳራ አለው::

ዛሬ ፕሮቴስታንቶች የሚቀበሏቸው የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ዝርዝር (የብሉይ ኪዳን ቀኖና) መሠረታቸው የተጣለው ከኢየሩሳሌም ውድቀትና በ70 ዓ.ም ከሆነው ከቤተ መቅደሱ መፍረስ በኋላ በሁለተኛው ምእተ ዓመት መባቻ ላይ ነው::

አይሁድ የብሉይ ኪዳንን መጻሕፍት ብዛት አስመልክተው፣ እስከ ጀምኒያው ጉባኤ (90ዓ.ም) ድረስ ይወያዩ ነበር:: ይህ የዕብራውያን ቀኖና የሰብዓ ሊቃናትን ትርጕም ትጠቀም በነበረው የጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ተቀባይነት አላገኘም:: በአንዳንድ የቤተ ክርስቲያን አበው ዘንድ፣ የትኞቹ መጻሕፍት ቀኖናውያት ናቸው፤ የትኞቹ ደግሞ አይደሉም የሚለው ፈጽሞ ጕዳይ አለመግባባትን ያስከተለ ቢሆንም እንኳ፣ አዋልድ መጻሕፍት እስከ ዘመነ ተሐድሶ ድረስ በብዙ ክርስቲያኖች ዘንድ ጥቅም ላይ ውለው ነበር:: በዚህ ወቅት አብዛኞቹ ወንጌላውያን አብያተ ክርስቲያናት ነባሩን የዕብራውያንን ቀኖና ለመከተል ሲወስኑ፣ የሮማዋ ቤተ ክርስቲያን በትሬንቱ ጉባኤ (1546 ዓ.ም) እንዲሁም በቅርቡ በተካሄደው የመጀመሪያው የቫቲካን ጉባኤ (1869-1870 ዓ.ም) ላይ፤ አዋልድ መጻሕፍትን የሚያጠቃልለውን፣ "የእስክንድርያውን" ቀኖና አጸደቀች::

አዋልድ መጻሕፍትን በመጀመሪያ ይጠቀሙባቸዋው የነበሩት ክርስቲያን ባለሥልጣኖች ቢሆኑም እንኳ፣ ይህን የሚያደርጉት መጻሕፍቱ ቀኖናውያት ናቸው ብለው አልነበረም::

ኢየሱስም ሆነ ሐዋርያት ከአዋልድ መጻሕፍት ጠቅሰው ማስተማራቸውን የሚያሳይ ግልጽ ማስረጃ የለም (ይሁዳ14 ማብ ይመ)። የጽሑፎቹ ባለቤት የሆነው የአይሁድ ኅብረተ ሰብ ጽሑፎቹን አልተቀበላቸውም። በሐዋርያት ሥራ ውስጥ በተመዘገቡት የሐዋርያት ስብከቶች ውስጥ እነዚህ ጽሑፎች የሚሸፍኑት ዘመን ቦታ ሳይሰጠው ተዘሎአል። እንዲያውም እንደ መጽሐፈ መቃብያን ቀዳማዊ ያሉ መጻሕፍት ብዙ የታሪክ ስሕተትና የጊዜ ቅደም ተከተል መፋለስ አለባቸው።

በቀኖናውያቱ መጻሕፍት የሚካተት፣ ፋይዳ ያለው ትምሀርት መለኮት በአዋልድ መጻሕፍት ውስጥ የለም። ይልቁንም ቀኖናውያት የሆኑትን መጻሕፍት የሚጻረሩ ትምህርቶች በአዋልዱ ውስጥ ይገኛሉ። ይሁን እንጂ፣ አዋልድ መጻሕፍት በሁለቱ ኪዳናት መካከል ያለውን ዘመን በተመለከተ ጠቃሚ መረጃዎችን የሚሰጡ መሆናቸው መዘንጋት የለበትም።

### የሙት ባሕር ጥቅልሎች

በ1947 ዓ.ም በጸደይ ወራት አንድ ዐረብ እረኛ፣ "የዘመኑ ታላቅ ጽሑፍ ግኝት" ተብሎ የሚጠራው ጥቅልል የተገኘበትን አንድ ዋሻ በሙት ባሕር ዳር ደቡብዊ ምዕራብ አቅጣጫ አየ። በዚህ አካባቢ ባሉ ዋሻዎች የተገኙ፣ "የሙት ባሕር ጥቅልሎች" የሚል ስያሜ የተሰጣቸው ጥቅልሎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትን፣ አቡቀለምሲሳዊ ሥራዎችን፣ ጥንታውያን የእምነት ዐርበኞችን ገድል የሚተርኩ ጽሑፎችንና እነዚህን ጽሑፎች ስለ ጻፉ ሰዎች የሚናገሩ ጽሑፎችን የሚያጠቃልሉ ናቸው።

በዚያ ስፍራ የተገኙት ጽሑፎች በግምት የመዝሙረ ዳዊት ሢሶ፣ አሪት ዘጻግም፣ በአዲስ ኪዳን መጻሕፍት በተደጋጋሚ ተጠቅሶ የሚገኘው ትንቢተ ኢሳይያስና ሌሎች ቅዱሳት መጻሕ ፍት ናቸው። አስደናቂ ከሆኑት ግኝቶች አንዱ 7.30 ሜትር ርዝመት ያለው የኢሳይያስ መጽሐፍ ጥቅልል ይገኝበታል።

እነዚህ ጥቅልሎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት አጻጻፍ እንዴት እንደ ሆነ ለማወቅ ተነሥቶ ሰነበረው ጥያቄ ዐይነተኛ መልስ ያስገኙ ሲሆኑ፣ ከዚህ በፊት ከሚታወቁት ቅጆች ይልቅ ከመጀመሪያው ጽሑፍ ጋር የ1000 ዓመት ቀረቤታ ያላቸውን ቅጆች የያዙ ናቸው። መጽሐፍ ቅዱስ የተጻፈባቸውን የዕብራይስጥና የአራማይክ ቋንቋዎች ለመረዳትና በኪዳናት መካከል የይሁዲነት ዕድገት እንዴት እንደ ነበር ለማወቅ ተችሎአል። ይህ ግኝት ሰመጽሐፍ ቅዱስ አንባብያን የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ቅጆች እንዴት ባለ ጥንቃቄ እንደ ተገለበጡና፣ በዚህም፣ቅጆቹ ያላቸውን አስተማማኝነት ለመገንዘብ ተጨባጭ መረጃ በመሆን ያገለግላል።

### የኅብረተ ሰብ እድገት

ኢየሱስ በአካል በምድር ሳለ ይታይ የነበረው ይሁዲነት (አይሁዳዊ እምነት) በአብዛኛው በሁለቱ ኪዳናት መካከል ባለው ጊዜ ውስጥ በተከሠተው ግፊት የመጣው ለውጥ ውጤት ነው።

### ዝርወተ እስራኤል

በምርኮ ዘመን የጀመረው የእስራኤላውያን መበተን የዘመኑ ጸሓፊ አይሁድ "ምድሩንና ባሕሩን" ሞሉት ብሎ እስከሚናገር ድረስ በፍጥነት ተከናውኖ ነበር።

ከፓለስቲና ውጭ የሚኖሩ፣ ከቤተ መቅደስ አምልኮ የተለዩት አይሁድ የራሳቸውን ሃይ ማኖታዊ ሥርዐት የቶራን መጽሐፍ በማንበብ፣ በምኩራቦቻቸው በመሰብሰብ ይፈጽሙ ነበር። የቀድሞዪቱ ቤተ ክርስቲያን የወንጌል መልእክተኞች ወደ ግሪክ ቋንቋ የተመለሰውን ብሉይ ኪዳን በመጠቀም ለሕዝብ የሚሰጡትን አገልግሎት በተበተኑት እስራኤላውያን መካከል ጀምረዋል።

### ሰዱቃውያን

በፓለስቲና የግሪኩ ዓለም አመለካከት በሰዱቃውያኑ ጕራ አማካይነት ተጽዕኖውን በሰፊው አሳድሮአል። በአብዛኛው የገገፁ መደብ የሚገኝበት ይህ ጕራ፣ የቤተ መቅደስ አካል ሆኗል፤ ካላቸው የሥልጣን ወንበር የተነሣ የፓለቲካውን ጕዳይ የሚቈጣጠሩ ናቸው።

በቍጥራቸው አነስተኛ ቢሆኑም፣ የፓለቲካ ሥልጣኑን በአብዛኛው የያዙ ስለ ሆኑ የሊ ቀ ካህንነቱም ሥልጣን ከእጃቸው አይወጣም ነበር። ከቶራ በስተቀር የየትኛውንም ሃይ ማኖታዊ ጽሑፍ ትምህርት (እንደ ሙታን ትንሣኤ ያለ)፣ በአምስቱ የሙሴ መጻሕፍት ውስጥ የማይ ገኘውን ሁሉ አይቀበሉም።

### ምኩራብ

በምርኮ ዘመን እስራኤል ከቤተ መቅደሱ ተለይታ መንግሥት የሌላትና በአረማውያን ገዢዎች አምልኮ የተከበበች ነበረች። እምነቷም ወደ መጥፋት ተቃርቦ ነበር። ይህን በመሰሉ ሁኔታዎች ውስጥ እያሉ በምርኮ ላይ የነበሩ አይሁድ የሃይማኖት ትኩረታቸውን ከአከባቢ ነገሮች ላይ እንሥተው ሳይጠፉ ወደ ቀሩት ነገሮች ማለትም ወደ ቶራና ወደ እግዚአብሔር ሕዝብነታቸው እምነት ራሳቸውን መልሰዋል። ስለ መንግሥታቸው ከማሰብ ይልቅ ስለ ሙሴ ሕግ፣ ስለ መቅደሱ ሥርዐቶች ከማሰብ ይልቅ ስለ ግል መንፈሳዊ ሕይወት ማሰብና መሥዋዕት በማቅረብ ፈንታ ጸሎት ላይ ማተኮር ጀመሩ።

ከምርኮ በሚመለስበት ጊዜ ይህን አዲስ የአምልኮ ዘይቤና በምኩራብ የመሰብሰብ ልማድ ይዘው መጡ፡ ይሁዲነቱም ቶራ ባለበት ስፍራ ሁሉ የሚተገበር ሆነ። የምኩራብ አምልኮ ዐይነተኛ ባሕርይ የሆነው በግል መንፈሳዊ ሕይወት ላይ እና ከእግዚአብሔር ጋር ባለ ኅብረት ላይ ማተኮር ይሁዲነት እንዳይጠፋ መርዳት ብቻ ሳይሆን፣ ለወንጌልም ጥርጊያ መንገድ አዘጋጅቶአል።

**ፈሪሳውያን**

ፈሪሳውያን የምኩራብ አለቆች የነበሩ ሲሆን የሙሴ ሕጋጋትን ለመተርጐም የሚጥሩ ናቸው። ከሙሴ ዘመን እንሥቶ በፍጥነት እየተለዋወጠ በመጣው ዓለም ውስጥ አይሁድ በእግዚአብሔር ፊት የቅድስና ሕይወት እንዲኖራቸውና ሕጉ እንዳይበረዝ የራሳቸውን ህጥር አበጅተውለት ነበር። ምንም እንኳ ቍጥራቸው አነስተኛና በብሔራዊ ጉዳይ ውስጥም ድርሻ ያልነበራቸው ቢሆኑም፣ ሐሳባቸው በሕዝቡ ዘንድ ተቀባይነት ነበረው። በ70 ዓ.ም. ቤተ መቅደሱ ሲፈርስ የቀሩት እነርሱ ብቻ ሲሆኑ፣ የዘመናዊው ይሁዲነት መንፈሳውያን አባቶች ናቸው።

**ኤሴናውያን**

የሙት ባሕር ጥቅልሎች እስከ ተገኙበት ጊዜ ድረስ ተረስቶ የቈየ የአይሁድ ክፍል
ሲሆን፣ በመቃብያን ዘመን በተፈጠረው ቀራኔ ራሳቸውን የለዩ አነስተኛ ቍጥር ያላቸው ሰዎች ቡድን ነበር። እንደ ፈሪሳውያን ሕግን መጠበቅ አስፈላጊ እንደ ሆነ ቢያምኑም፣ በቤተ መቅደሱ ያለው ክህነታዊ አገልግሎት የተበላሸ እንደ ሆነ ይቈጥራሉ፤ የመቅደሱንም ሥርዐትና መሥዋዕት ማቅረቡንም አይቀበሉም ነበር። በአያሌ የጥንት ጸሐፍት እንደ ተገለጸው ትክክለኛው የኤሴናውያን ባሕርይ ባይታወቅም የሙት ባሕር ጥቅልሎች በመባል የሚታወቀውን ያዘጋጀው የቍምራን "ማኅበረ ሰብ የኤሴናውያን ቡድን እንደ ሆነ የሚጠቁም አጠቃላይ ስምምነት አለ።

ኤሴናውያን እውነተኞቹ ትሩፋን እነርሱ እንደ ሆኑ ስለሚያምኑ፣ በአብዛኛው ራሳቸውን ከይሁዲነት ለይተው ለግል መንፈሳዊ ሕይወት ንጽሕናና "የብርሃን ልጆች ከጨለማ ልጆች"ጋር ለሚያደርጉት የመጨረሻ ጦርነት ራሳቸውን የሚያዘጋጁ ነበሩ። ቀደምት "የ ጽድቅ መምህሮቻቸውን" በመመልከት ከአቡቀለምሲሳዊ የእምነት ልምምዳቸው የተነሣ የሁለት ወይም የሦስት መሲሖችን መምጣት ይጠባበቁ ነበር። ሆኖም በ70 ዓ.ም. የሆነው የቤተ መቅደሱ መፍረስ ተስፋቸው የተሟጠጠ እንዲመስል አድርጎታል።

የቍምራን ማኅበረ ሰብን እምነቶች ከክርስትና እምነት ጅማሬ ጋር እኩል ለማድረግ ሙከራዎች ተደርገዋል። አንዳንዶች ኢየሱስን "የጽድቅ መምህሮቻቸው" አምሳያ እንደ ሆነ አድርገው ይወስዱታል፤ እንዲያውም መጥምቁ ዮሐንስንና ኢየሱስን በዚህ ቡድን ውስጥ አባላት እንደ ሆኑ ይቈጥራሉ። ሆኖም ለእነዚህ ግምቶች ትክክለኛ ማረጋገጫ የለም።

## የወንጌላት ስምምነት

| | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ | ዮሐንስ |
|---|---|---|---|---|
| **ለኢየሱስ ማንነት አጭር መግለጫ** | | | | |
| ሉቃስ መልእክቱን የጻፈበት ዐላማ | | | 1፥1-4 | |
| የዮሐንስ መግቢያ፦ ኢየሱስ ክርስቶስ ትስብእት የሆነ ዘላለማዊ ቃል | | | | 1፥1-18 |
| የኢየሱስ ሕጋዊ ዘርዐ ትውልድ በዮሴፍ፤ እንዲሁም ከማርያም ማሕፀን መውጣቱ | 1፥1-17 | | 3፥23-38 | |
| **የመጥምቁ ዮሐንስ የልጅነት ዘመን** | | | | |
| ዮሐንስ እንደሚወለድ ለዘካርያስ ትንቢት ተነገረው | | | 1፥5-25 | |
| ኢየሱስ እንደሚወለድ ለማርያም ትንቢት ተነገራት | | | 1፥26-38 | |
| ማርያም ኤልሳቤጥን መጎብኘቷና የኤልሳቤጥ መዝሙር | | | 1፥39-45 | |
| የማርያም የደስታ መዝሙር | | | 1፥46-56 | |
| የዮሐንስ መወለድ | | | 1፥57-66 | |
| የዘካርያስ ትንቢታዊ መዝሙር | | | 1፥67-79 | |
| የዮሐንስ እድገትና የልጅነት ዘመኑ | | | 1፥80 | |
| **የኢየሱስ ክርስቶስ የልጅነት ዘመን** | | | | |
| የኢየሱስ እንደሚወለድ ለዮሴፍ ተነገረው | 1፥8-25 | | | |
| የኢየሱስ መወለድ | | | 2፥1-7 | |
| የመላእክት ምስጋናና የእረኞች ምስክርነት | | | 2፥8-20 | |
| የኢየሱስ መገረዝ | | | 2፥21 | |
| ኢየሱስ ለስምዖንና ለሐና ለመታየት ወደ ቤተ መቀደስ ሄደ | | | 2፥22-38 | |
| የሰብአ ሰገል መጎብኘት (የምሥራቅ ጠቢባን ኢየሱስን መጐብኘት) | 2፥1-12 | | | |
| ወደ ግብፅ መሸሽና በቤተልሔም የሕፃናት መገደል | 2፥13-18 | | | |
| ወደ ናዝሬት መመለስ | 2፥19-23 | | 2፥39 | |
| የኢየሱስ እድገትና የልጅነት ዘመን | | | 2፥40 | |
| ኢየሱስ የፋሲካን በዓል ለማክበር ለመጀመሪያ ጊዜ ወደ ኢየሩሳሌም መሄዱ | | | 2፥41-50 | |
| የኢየሱስ እድገት | | | 2፥51-52 | |
| **የመጥምቁ ዮሐንስ የአደባባይ አገልግሎት** | | | | |
| አገልግሎቱን መጀመሩ | | 1፥1 | 3፥1-2 | |
| ማንነቱ፣ ስብከቱና ማጥመቁ | 3፥1-6 | 1፥2-6 | 3፥3-6 | |
| ለፈሪሳውያን፣ ለሰዱቃውያን፣ ለሕዝቡ፣ ለቀረጥ ሰብሳቢዎችና ለወታደሮች የነበረው መልእክት | 3፥7-10 | | 3፥7-14 | |
| ስለ ክርስቶስ የነበረው ገለጻ | 3፥11-12 | 1፥7-8 | 3፥15-18 | |
| **የዮሐንስ አገልግሎት ማብቂያና የክርስቶስ የአደባባይ አገልግሎት ጅማሬ** | | | | |
| የኢየሱስ በዮሐንስ መጠመቅ | 3፥13-17 | 1፥9-11 | 3፥21-23 | |
| ኢየሱስ በምድረ በዳ መፈተን | 4፥1-11 | 1፥12-13 | 4፥1-13 | |
| ዮሐንስ ስለ ራሱ ለካህናትና ለሌዋውያን የሰጠው ምስክርነት | | | | 1፥19-28 |
| ዮሐንስ፣ ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ ለመሆኑ የሰጠው ምስክርነት | | | | 1፥29-34 |
| የመጀመሪያዎቹ የኢየሱስ ታምር፦ ውሃውን ወደ ወይን ጠጅ መቀየሩ | | | | 2፥1-11 |
| ኢየሱስ ለመጀመሪያ ጊዜ ከእናቱ፣ ከወንድሞቹና ከመጀመሪያዎቹ ደቀ መዛሙርቱ ጋር ወደ ቅፍርናሆም ሄደ | | | | 2፥12 |
| በፋሲካ በዓል ጊዜ የተደረገ የመጀመሪያው ቤተ መቅደስን ማንጻት | | | | 2፥13-22 |
| ለኢየሱስ ታምራት ሰዎች የነበራቸው የመጀመሪያው ምላሽ | | | | 2፥23-25 |
| ኒቆዲሞስ ለኢየሱስ ያደረገው ቃለ መጠይቅ | | | | 3፥1-21 |
| ዮሐንስ በኢየሱስ መተካቱ | | | | 3፥22-36 |
| ኢየሱስ የይሁዳን ምድር ትቶ መሄዱ | 4፥12 | 1፥14 | 3፥19-20፤4፥14 | 4፥1-4 |
| ከሳምራዊቷ ሴት ጋር የተደረገ ውይይት | | | | 4፥5-26 |
| የመንፈሳዊ መከር ተግዳሮቶች | | | | 4፥27-38 |
| በሲካር የተካሄደ የወንጌል ሥርጭት | | | | 4፥39-42 |
| የኢየሱስ ገሊላ መድረስ | | | | 4፥43-45 |
| **የኢየሱስ ክርስቶስ የገሊላ አገልግሎቱ** | | | | |
| *ተቃውሞ ከቤት ተነሣ፤ አዲስ የአገልግሎት በር ተከፈተ* | | | | |
| የገሊላው አገልግሎት ባሕርይ | 4፥17 | 1፥14-15 | 4፥14-15 | |
| ኢየሱስ በቃና ሆኖ በቅፍርናሆም የነበረውን ልጅ መፈወሱ | | | | 4፥46-54 |
| ተቃውሞና አገልግሎት በናዝሬት | | | 4፥16-31 | |
| ወደ ቅፍርናሆም መዛወር | 4፥13-16 | | | |

## የወንጌላት ስምምነት

| | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ | ዮሐንስ |
|---|---|---|---|---|
| ***የደቀመዛሙርት መጠራትና አገልግሎት በገሊላ ምድር*** | | | | |
| የአራቱ መጠራት | 4፥18-22 | 1፥16-20 | 5፥1-11 | |
| በቅፍርናሆም ምኩራቦች የተሰጠው ትምህርት አጋንንትን በማስወጣት እውነተኛነቱ ተረጋገጠ | | 1፥21-28 | 4፥31-37 | |
| የጴጥሮስ ዐማትና ሌሎች ተፈወሱ | 8፥14-17 | 1፥29-34 | 4፥38-41 | |
| ከስምዖንና ከሌሎች ጋር ወደ ገሊላ የተደረገ ጉዞ | 4፥23-25 | 1፥35-39 | 4፥42-44 | |
| የለምጻሙ መንጻትና ነገሩ በአደባባይ መታወቁ | 8፥2-4 | 1፥40-45 | 5፥12-16 | |
| ሽባው ይቅርታን ማግኘቱና መፈወሱ | 9፥1-8 | 2፥1-12 | 5፥17-26 | |
| የማቴዎስ መጠራት | 9፥9 | 2፥13-14 | 5፥27-28 | |
| በማቴዎስ ቤት የተደረገው ግብዣ | 9፥10-13 | 2፥15-17 | 5፥29-32 | |
| ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱ ለምን እንደማይጾሙ በሦስት ምሳሌዎች ገለጸ | 9፥14-17 | 2፥18-22 | 5፥33-39 | |
| ***ሰንበትን በተመለከተ የተነሣ ክርክር*** | | | | |
| ኢየሱስ በሰንበት ቀን ፈወሰ | | | | 5፥1-9 |
| ኢየሱስ ራሱን ከእግዚአብሔር ጋር እኩል በማድረጉና ሰንበትን በመሻሩ ለመግደል የተደረገ ሙከራ | | | | 5፥10-18 |
| ወልድ ከአብ ጋር እኩል መሆኑን ለማስረገጥ የተሰጠ ትምህርት | | | | 5፥19-47 |
| ደቀ መዛሙርት በሰንበት ቀን እሸት በመቅጠፋቸው ምክንያት የተነሣ ክርክር | 12፥1-8 | 2፥23-28 | 6፥1-5 | |
| እጁ የሰለለችበት ሰው በሰንበት ቀን ተፈወሰ | 12፥9-14 | 3፥1-6 | 6፥6-11 | |
| ከብዙ ስፍራ ካመጡ እጅግ ብዙ ሰዎች ጋር ወደ ገሊላ ባሕር ሄደ | 12፥15-21 | 3፥7-12 | | |
| ***የዐሥራ ሁለቱ መመረጥና የተራራው ስብከት*** | | | | |
| የዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት መመረጥ | | 3፥13-19 | 6፥12-16 | |
| የስብከቱ ቦታ | 5፥1-2 | | 6፥17-19 | |
| መንግሥተ ሰማያት የሚወርሱ ሰዎች በረከትና የማይወርሱ ሰዎች ወዮታ | 5፥3-12 | | 6፥20-26 | |
| መንግሥቱን ለሚጠባበቁ የተሰጣቸው ኀላፊነት | 5፥13-16 | | | |
| ሕግ፣ ጽድቅና መንግሥተ ሰማያት | 5፥17-20 | | | |
| የሕግን አተረጓጎም በተመለከተ ስድስት ንጽጽሮች | 5፥21-48 | | 6፥27-30:32-36 | |
| የጽድቅን ሥራ በተመለከተ ሊወገዱ የሚገባቸው ሦስት "የግብዝነት" | 6፥1-18 | | | |
| ሀብት፣ ተገቢ ያልሆነ ፍርድና የተቀደሱትን ነገሮች አግባብ ባልሆነ መንገድ መጠቀም የሚከለክሉ ሦስት እገዳዎች | 6፥19-7፥6 | | 6፥37-42 | |
| የሕይወት ተዛምዶና ድምዳሜ | 7፥7-27 | | 6፥31:43-49 | |
| የሕዝቡ ምላሽ | 7፥28-8፥1 | | | |
| ***የዝናው መጨመርና ንስሐን አጽንዖት ሰጥቶ ማስተማሩ*** | | | | |
| የመቶ አለቃው እምነትና የአገልጋዩ መፈወስ | 8፥5-13 | | 7፥1-10 | |
| በናይን ከተማ የመበለቲቱ ልጅ ከሞት መነሣት | | | 7፥11-17 | |
| መጥምቁ ዮሐንስ ከእግዚአብሔር መንግሥት ጋር ያለው ግንኙነት | 11፥2-19 | | 7፥18-35 | |
| ኮራዚና ቤተ ሳይዳ ንስሐ ባለመግባታቸው ወዮ ተባለላቸው | 11፥20-30 | | | |
| በኀጢአቷ እጅግ ባዘነች ሴት የክርስቶስ እግር በሽቱ ተቀባ | | | 7፥36-50 | |
| ***የአይሁድ መሪዎች የመጀመሪያው የአደባባይ ተቃውሞ*** | | | | |
| ከዐሥራ ሁለቱና ከሌሎቹ ደቀ መዛሙርት ጋር የተደረገ ጉዞ | | | 8፥1-3 | |
| የሕግ መምህራንና ፈሪሳውያን በጽርፈት ተወነጀሉ | 12፥22-37 | 3፥20-30 | | |
| ምልክት ለማየት የተቀረበው ጥያቄ ተቀባይነት አለማግኘት | 12፥38-45 | | | |
| አዲስ ስለ ሆነው መንፈሳዊ ዝምድና የቀረበው ንግግር | 12፥46-50 | 3፥31-35 | 8፥19-21 | |
| ***ስለ እግዚአብሔር መንግሥት ምስጢር የቀረቡ ምሳሌዎች በባሕሩ አጠገብ ለሕዝቡ የተነገሩ*** | | | | |
| የምሳሌዎቹ መቼት (ምሳሌዎቹ የተነገሩበት ቦታ፣ ጊዜና ሁኔታ) | 13፥1-3 | 4፥1-2 | 8፥4 | |
| የዘሪው ምሳሌ | 13፥3-23 | 4፥3-25 | 8፥5-18 | |
| በግብታዊነት የሚያድገው ዘር ምሳሌ | | 4፥26-29 | | |
| የእንክርዳዱ ምሳሌ | 13፥24-30 | | | |
| የሰናፍጩ ዘር ምሳሌ | 13፥31-32 | 4፥30-32 | | |
| የእርሾው ምሳሌ | 13፥33-35 | 4፥33-34 | | |
| ***በቤት ውስጥ ለደቀ መዛሙርት የተነገሩ*** | | | | |
| የእንክርዳዱ ምሳሌ ፍቺ | 13፥36-43 | | | |
| የተደበቀው ሀብት ምሳሌ | 13፥44 | | | |
| የከበረው የዕንቁ ምሳሌ | 13፥45-46 | | | |

## የወንጌላት ስምምነት

| | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ | ዮሐንስ |
|---|---|---|---|---|
| የመረቡ ምሳሌ | 13፥47-50 | | | |
| የቤቱ ባለቤት ምሳሌ | 13፥51-53 | | | |
| ***የተቃውሞው መቀጠል*** | | | | |
| ባሕሩን ማቋረጥና ማዕበሉን ጸጥ ማድረግ | 8፥18:23-27 | 4፥35-41 | 8፥22-25 | |
| በጌርጌሴኖን አገር አጋንንት ያደሩባቸው ሁለት ሰዎች መፈወሳቸውና ፈውሱ ያስከተለው ተቃውሞ | 8፥28-34 | 5፥1-20 | 8፥26-39 | |
| ወደ ገሊላ መመለሱ፣ የኢየሱስን ልብስ ዳሳ የተፈወሰችው ሴትና የኢያኢሮስ ሴት ልጅ ከሞት መነሣቷ | 9፥18-26 | 5፥21-43 | 8፥40-56 | |
| ሦስት የፈውስ ታምራትና ዳግም እግዚአብሔርን ስለመጻረፍ የቀረበ ክስ | 9፥27-34 | | | |
| ወደማታምነው ናዝሬት የተደረገ የመጨረሻ ጉዞ | 13፥54-58 | 6፥1-6 | | |
| ***የመጨረሻው የገሊላ ስብሰባ*** | | | | |
| የሠራተኞች ማነስ | 9፥35-38 | 6፥6 | | |
| የዐሥራ ሁለቱ ተልእኮ | 10፥1-42 | 6፥7-11 | 9፥1-5 | |
| የሠራተኞች መላክ | 11፥1 | 6፥12-13 | 9፥6 | |
| ሄሮድስ ስለ ኢየሱስ ማንነት የነበረው የተሳሳተ ግንዛቤ | 14፥1-2 | 6፥14-16 | 9፥7-9 | |
| የመጥምቁ ዮሐንስ መታሰርና ዘመንና ዐንገቱ ስለመቀላቱ | 14፥3-12 | 6፥17-29 | | |
| **የክርስቶስ አገልግሎት በገሊላ አካባቢ** | | | | |
| ***ስለ ሕይወት እንጀራ የተሰጠ ትምህርት*** | | | | |
| የሠራተኞቹ መመለስ | | 6፥30 | 9፥10 | |
| ከገሊላ ወጥቶ መሄድ | 14፥13-14 | 6፥13-34 | 9፥10-11 | 6፥1-3 |
| አምስት ሺህ ሰዎችን መመገቡ | 14፥15-21 | 6፥35-44 | 9፥12-17 | 6፥4-13 |
| ኢየሱስን ንጉሥ ለማድረግ ተሞክሮ በእንጭ ጭንቱ የተቀጨው ሙከራ | 14፥22-23 | 6፥45-46 | | 6፥14-15 |
| የባሕሩ ማዕበል በተነሣ ጊዜ በውሃው ላይ መራመዱ | 14፥24-33 | 6፥47-52 | | 6፥16-21 |
| በጌንሴሬጥ የተደረገ ፈውስ | 14፥34-36 | 6፥53-56 | | |
| ስለ ሕይወት እንጀራ የተሰጠ ትምህርት | | | | 6፥22-59 |
| ከደቀ መዛሙርት መካከል አንዳንዱ ወደ ኋላ አፈገፈገ | | | | 6፥60-71 |
| ***ከፈሪሳውያን፣ ከሰዱቃውያንና ከሄሮድስ ሰዎች እርሾ ስለመጠበቅ*** | | | | |
| አለመንጻትን በተመለከተ በትውፊት ላይ የተደረገ ክርክር | 15፥1-3:7-9:<br>3-6:10-20 | 7፥1-23 | | 7፥1 |
| በጢሮስና በሲዶና አገር ያመነችው ግሪካዊት ሴት | 15፥21-28 | 7፥24-30 | | |
| በዐሥሩ ከተሞች የተደረገ ፈውስ | 15፥29-31 | 7፥31-37 | | |
| አራት ሺህ ሰዎችን በዐሥሩ ከተሞች መመገቡ | 15፥32-38 | 8፥1-9 | | |
| ወደ ገሊላ መመለሱና ከፈሪሳውያንና ከሰዱቃውያን ጋር መገናኘቱ | 15፥39-16፥4 | 8፥9-12 | | |
| ለፈሪሳውያን፣ ለሰዱቃውያንና ለሄሮድስ ሰዎች የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | 16፥5-12 | 8፥13-21 | | |
| ዐይነ ሥውሩን በቤተ ሳይዳ መፈወሱ | | 8፥22-26 | | |
| ***ስለ መሲሑ የተሰጠ ትምህርትና የትምህርቱ አጽንዖት*** | | | | |
| ጴጥሮስ ኢየሱስ መሲሑ መሆኑን ማወቁና ለቤተ ክርስቲያን የተነገረው የመጀመሪያው ትንቢት | 16፥13-20 | 8፥27-30 | 9፥18-21 | |
| ስለ መነቀፉ፣ ስለ መሰቀሉና ስለ ትንሣኤው ለመጀመሪያ በቀጥታ የተነገረ ትንቢት | 16፥21-26 | 8፥31-37 | 9፥22-25 | |
| የሰው ልጅ ምዕጽአትና ፍርድ | 16፥27-28 | 8፥38-9፥1 | 9፥26-27 | |
| የኢየሱስ መለወጥ | 17፥1-8 | 9፥2-8 | 9፥28-36 | |
| ትንሳኤን፣ ኤልያስንና መጥምቁ ዮሐንስን በተመለከተ የተነሣ ክርክር | 17፥9-13 | 9፥9-13 | 9፥36 | |
| ***ሌሎች ሰዎችን በተመለከተ የተሰጠ ኀላፊነት*** | | | | |
| ጋኔን ያደረበት ልጅ መፈወሱና ስለ አለማመን የቀረበ ተግሣጽ | 17፥14-20 | 9፥14-29 | 9፥37-43 | |
| ስለ ኢየሱስ ሞትና ትንሣኤ የተነገረ ሁለተኛ ትንቢት | 17፥24-27 | 9፥30-32 | 9፥43-45 | |
| ለቤተ መቅደስ የሚከፈል ግብር | 17፥24-27 | | | |
| በመንግሥተ ሰማይ የእኔ እበልጥ ፉክክር | 18፥1-5 | 9፥33-37 | 9፥46-48 | |
| ለኀጢአት ምክንያት ስለሚሆኑ ነገሮች የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | 18፥6-14 | 9፥38-50 | 9፥49-50 | |
| ወንድምን የማስናከል ኀጢአት ይቅርታና መፍትሔው | 18፥15-35 | | | |
| ***ለዳስ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም የተደረገ ጉዞ*** | | | | |
| ከደቀ መዛሙርት የሚጠበቅ ፍጹም መስጠት | 8፥19-22 | | 9፥57-62 | |
| የኢየሱስ ወንድሞች ፌዝ | | | | 7፥2-9 |
| በሰማርያ በኩል የተደረገ ጉዞ | | | 9፥51-56 | 7፥10 |

## የወንጌላት ስምምነት

| | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ | ዮሐንስ |
|---|---|---|---|---|
| **ክርስቶስ በይሁዳ ያገለገለባቸው የኋለኞች ጊዜያት** | | | | |
| ***በዳስ በዓል የጀመረው አገልግሎት*** | | | | |
| የኢየሱስ ትምህርትና ታምር ያስከተሏቸው የተለያዩ ውጤቶች | | | | 7፥11-31 |
| ኢየሱስን ለመያዝ የተደረገ ሙከራ | | | | 7፥32-52 |
| ኢየሱስ በዝሙት የተያዘችውን ሴት ይቅር አለ | | | | (7፥53-8፥11) |
| ኢየሱስ የዓለም ብርሃን ነኝ ማለቱ ያስነሣው ክርክር | | | | 8፥12-20 |
| ኢየሱስ ክርስቶስ ከአብ ጋር ያለው ግንኙነት | | | | 8፥21-30 |
| ኢየሱስ ከአብርሃም ጋር የነበረው ግንኙነትና በድንጋይ ለመውገር የተደረገው ሙከራ | | | | 8፥31-59 |
| ከመወለዱ ጀምሮ ዐይነ ሥውር የነበረው ሰው | | | | 9፥1-7 |
| የዐይነ ሥውሩ ጎረቤቶች ምላሽ | | | | 9፥8-12 |
| ፈሪሳውያን በዐይነ ሥውሩ ሰው ላይ ያደረጉት ምርመራና ማባረር | | | | 9፥13-34 |
| ኢየሱስ ለዕውሩ ሰው ራሱን አስተዋወቀ | | | | 9፥35-38 |
| የፈሪሳውያን መንፈሳዊ ዕውርነት | | | | 9፥39-41 |
| ስለ መልካም እረኛና ሌባ | | | | 10፥1-18 |
| በአይሁዶች መካከል የተካሄደው ተጨማሪ ክፍፍል | | | | 10፥19-21 |
| ***ስለ ፍቅር አገልግሎትና ስለ ጸሎት ለግለሰቦች የተሰጠ ትምህርት*** | | | | |
| የሰባዎቹ ተልእኮ | | | 10፥1-16 | |
| የሰባዎቹ መመለስ | | | 10፥17-24 | |
| የደጉ ሳምራዊ ታሪክ | | | 10፥25-37 | |
| ኢየሱስ ማርያምንና ማርታን ጎበኘ | | | 10፥38-42 | |
| ስለ ጸሎት የተሰጠ ትምህርትና የግልጹ ወዳጅ ታሪክ | | | 11፥1-3 | |
| ***ከሕግ መምህራንና ከፈሪሳውያን ጋር የተደረገ ሁለተኛ ክርክር*** | | | | |
| እግዚአብሔርን የመጻረፍ ሦስተኛው ክስና ሁለተኛው ክርክር | | | 11፥14-36 | |
| ከፈሪሳዊው ጋር እየበላ ለፈሪሳውያንና ለሕግ መምህራን ወዮ አለ | | | 11፥37-54 | |
| ለደቀ መዛሙርት ስለ ግብዝነት የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | | | 12፥1-12 | |
| የሰው ልጅን ምጽአት ተዘጋጅቶ ባለመጠበቅ ላይ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | | | 12፥35-48 | |
| ስለሚመጣው ክፍፍል የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | | | 12፥49-53 | |
| የአሁኑን ጊዜ ባለ መለየት የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | | | 12፥54-59 | |
| ሁለቱ አማራጮች:- ንስሓ መግባት ወይም መጥፋት | | | 13፥1-9 | |
| አንዲት ሴት በሰንበት ቀን ስለ ተፈወሰች የምኵራብ አለቆች ያስነሡት ተቃውሞ | | | 13፥10-21 | |
| በቤተ መቅደስ መታደስ በዓል ኢየሱስ እግዚአብሔርን ተዳፍሯል በሚል እርሱን ለማሰር ወይም በድንጋይ ለመውገር የተደረገ ሙከራ | | | | 10፥22-39 |
| **ብፔሪያና አካባቢው የክርስቶስ አገልግሎት** | | | | |
| ***የደቀ መዝሙርነት መርሆች*** | | | | |
| ከኢየሩሳሌም እስከ ፔሪያ | | | | 10፥40-42 |
| ስለ ድነትና መንግሥተ ሰማይ ስለ መግባት የቀረበ ጥያቄ | | | 13፥22-30 | |
| የኢየሱስ ሞት መቃረብና ለኢየሩሳሌም ያዘነው ሐዘን | | | 13፥31-35 | |
| ኢየሱስ በሰንበት ቀን ከፈሪሳውያን አለቆች ወደ አንዱ ቤት ምሳ ሲበላ ሰውነቱ የሚያብጥበትን ሰው መፈወሱና በዚያን ወቅት የተናገራቸው ሦስት ምሳሌዎች | | | 14፥1-24 | |
| ደቀ መዝሙር ሊከፍለው የሚገባው ዋጋ | | | 14፥25-35 | |
| ከኀጢአተኞች ጋር ኅብረት ማድረግ ተገቢ እንደ ሆነ ለማሳየት የተሰጠ ምሳሌ | | | 15፥1-32 | |
| ገንዘብን በተገቢው መንገድ ስለመጠቀም የተሰጠ ምሳሌ | | | 16፥1-13 | |
| ስለ ገንዘብ አደገኝነት ለማስተማር የተሰጠ ታሪክ | | | 16፥14-31 | |
| ስለ ደቀ መዛሙርነት የተሰጡ አራት ትምህርቶች | | | 17፥1-10 | |
| የአልዓዛር መታመምና መሞት | | | | 11፥1-16 |
| የአልዓዛር ከሞት መነሣት | | | | 11፥17-44 |
| ሸንጎው ኢየሱስ እንዲሞት በየነ | | | | 11፥45-54 |
| ***ወደ ኢየሩሳሌም ለመጨረሻ ጊዜ በሚሄድበት ወቅት ያስተማረው ትምህርት*** | | | | |
| በሰማርያና በገሊላ በኩል ሲያልፍ ዐሥር ለምጻሞችን ፈወሰ | | | 17፥11-21 | |
| የሰው ልጅ ምጽአትን/በተመለከተ የተሰጠ ትምህርት | | | 17፥22-37 | |
| ስለ ጸሎት፣ የተሰጡ ሁለት ምሳሌዎች:- ድኻዋ መበለትና ዐመፀኛው ዳኛ እንዲሁም ፈሪሳዊውና ቀረጥ ሰብሳቢው | | | 18፥1-14 | |
| በስስታምነትና በገንዘብ ስለ መመካት የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | | | 12፥13-34 | |

## የወንጌላት ስምምነት

| | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ | ዮሐንስ |
|---|---|---|---|---|
| ከፈሪሳውያን የፍቺ ትምህርት ጋር የተደረገ ፍጥጫ | 19፥1-12 | 10፥1-12 | | |
| መንግሥተ ሰማይን በተመለከተ የሕፃናት ምሳሌ | 19፥13-15 | 10፥13-16 | 18፥15-17 | |
| መንግሥተ ሰማይና ባለ ጠግነት | 19፥16-30 | 10፥17-31 | 18-18-30 | |
| የመሬት ባለቤቱ ሉዓላዊነት ምሳሌ | 20፥1-16 | | | |
| ስለ ክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ የተነገረው ሦስተኛው ትንቢት | 20፥17-19 | 10፥32-34 | 18፥31-34 | |
| ከፍ ማለትን ለሚፈልጉ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ | 20፥20-28 | 10፥35-45 | | |
| በርጤሜዎስና ጓደኛው ተፈወሱ | 20፥29-34 | 10፥46-52 | 18፥35-43 | |
| የዘኬዎስ መዳን | | | 19፥1-10 | |
| መንግሥተ ሰማይ በምትዘገይባት ጊዜ ኀላፊነትን ስለመወጣት የተሰጠ ምሳሌ | | | 19፥11-28 | |
| **ኢየሱስ በክብር ወደ ኢየሩሳሌም መግባቱና የበለሲቱ ዛፍ** | | | | |
| ቢታንያ ደረሰ | | | | 11:55-12፥1: 9-11 |
| በክብር ወደ ኢየሩሳሌም መግባቱ | 21፥1-3:6-7: 4-5:8-11: 14-17 | 11፥1-11 | 19፥29-44 | 12፥12-19 |
| ፍሬ ስለሌላት የተረገመችው የበለስ ዛፍ | 21፥18-19 | 11፥12-14 | | |
| ቤተ መቅደስን ዳግም ማጽዳቱ | 21፥12-13 | 11፥15-18 | 19፥45-48 | |
| ጥቂት ግሪካውያን ኢየሱስን ለማየት ያቀረቡት ጥያቄና የሰው ልጅ ከፍ ከፍ የማለቱ አስፈላጊነት | | | | 12፥20-36 |
| ሰዎች ስለ ኢየሱስ የነበራቸው የተለያዩ ምላሾችና ኢየሱስ ስለ ሕዝቡ የነበረው ምላሽ | | | | 12፥36-50 |
| የበለሲቱ ዛፍ መድረቅና ስለ እምነት የተሰጠ ትምህርት | 21፥19-22 | 11፥19-25 | 21፥37-38 | |
| ***ስለ ክርስቶስ ባለ ሥልጣንነት በግልጽ የቀረበ ጥያቄ*** | | | | |
| የኢየሱስ ክርስቶስን ሥልጣን በተመለከተ ካህናት፣ የሕግ መምህራንና ሽማግሌዎች የጠየቁት ጥያቄ | 21፥23-27 | 11፥27-33 | 20፥1-8 | |
| ኢየሱስ ለራሱ ጥያቄ የመለሰው መልስና ሦስቱ ምሳሌዎች | 21፥28-22፥14 | 12፥1-12 | 20፥9-19 | |
| ኢየሱስን ለማጥመድ ፈሪሳውያንና የሄሮድስ ሰዎች ለቄሳር ቀረጥ ስለ መክፈል የጠየቁት ጥያቄ | 22፥15-22 | 12፥13-17 | 20፥20-26 | |
| ትንሣኤን አስመልክቶ ሰዱቃውያን ግራ የተጋቡበት ጥያቄ | 22፥23-33 | 12፥18-27 | 20፥27-40 | |
| የፈሪሳውያን ሕጋዊ ጥያቄ | 22፥34-40 | 12፥28-34 | | |
| ***ለጠላቶቹ ተግዳሮት ኢየሱስ የመለሰው መልስ*** | | | | |
| እንደ ልጅና እንደ ጌትነቱ ኢየሱስ ከዳዊት ጋር የነበረው ግንኙነት | 22፥41-46 | 12፥35-37 | 20፥41-44 | |
| የሕግ መምህራንንና ፈሪሳውያንን በተመለከተ የቀረቡ ሰባት ወዮታዎች | 23፥1-36 | 12፥38-40 | 20፥45-47 | |
| ኢየሱስ ለኢየሩሳሌም ያዘነው ሐዘን | 23፥37-39 | | | |
| ድኻዋ መበለት ያላትን ሁሉ ሰጠች | | 12፥41-44 | 21፥1-4 | |
| **ስለ ክርስቶስ ሞት የተነገሩ ትንቢቶች** | | | | |
| ***የደብረ ዘይት ተራራ ትምህርት:- ኢየሱስ ስለ ቤተ መቅደሱና ስለ ዳግም ምጽአቱ የተናገረው ትንቢት*** | | | | |
| ትምህርቱ የተሰጠበት ቦታና ጊዜ (መቼት) | 24፥1-3 | 13፥1-4 | 21፥5-7 | |
| የምጥ ጣር መጀመሪያ | 24፥4-14 | 13፥5-13 | 21፥8-19 | |
| የጥፋት እርኵሰትና የኋለኛው ጭንቀት | 24፥15-28 | 13፥14-23 | 21፥20-24 | |
| የሰው ልጅ ምጽአት | 24፥29-31 | 13፥24-27 | 21፥25-27 | |
| የቀረቤታው ምልክቶች ነገር ግን የጊዜው አለመታወቅ | 24፥32-41 | 13፥28-32 | 21፥28-33 | |
| ነቅቶ ስለ መጠበቅና ስለ ታማኝነት የተሰጡ አምስት ምልክቶች | 24፥42-25፥30 | 13፥33-37 | 21፥34-36 | |
| የሰው ልጅ በሚመጣበት ጊዜ የሚሆነው ፍርድ | 25፥31-46 | | | |
| ***አሳልፎ ለመስጠት የተደረገ ዝግጅት*** | | | | |
| ኢየሱስን ለማሰርና ለመግደል የሸንጎው ሤራ | 26፥1-5 | 14፥1-2 | 22፥1-2 | |
| ማርያም ኢየሱስን ለሞቱ ሽቱ መቀባቷ | 26፥6-13 | 14፥3-9 | | 12፥2-8 |
| ይሁዳ ኢየሱስን አሳልፎ ለመስጠት መስማማቱ | 26፥14-16 | 14፥10-11 | 23፥3-6 | |
| ***የመጨረሻው ራት*** | | | | |
| የፋሲካ መብል ዝግጅት | 26፥17-19 | 14፥12-16 | 22፥7-13 | |
| የፋሲካው መብል ጅማሬና ታላቅነትን አስመልክቶ በደቀ መዛሙርት መካከል የተደረገ ክርክር | 26፥20 | 14፥17 | 22፥14-16፥24-30 | |
| የደቀ መዛሙርቱን እግር አጠበ | | | | 13፥1-20 |
| አሳልፎ የሚሰጠው መታወቅ | 26፥21-25 | 14፥18-21 | 22፥21-23 | 13፥21-30 |

ረ. በቅፍርናሆምና በናይን የተሠሩ ታምራት (7፥1-18)
ሰ. የመጥምቁ ዮሐንስ ጥያቄ (7፥19-29)
ሸ. ኢየሱስና ፈሪሳውያን (7፥30-50)
ቀ. ገሊላ ውስጥ ለሁለተኛ ጊዜ መዘዋወሩ (8፥1-3)
በ. ስለ እግዚአብሔር መንግሥት የተነገሩ ምሳሌዎች (8፥4-21)
ተ. በገሊላ ባሕር ማዶ የተደረገው ጉዞ (8፥22-39)
ቸ. ገሊላ ውስጥ ለሦስተኛ ጊዜ መዘዋወሩ (8፥40-9፥9)
5. ገሊላ አካባቢ ወዳሉት ስፍራዎች መሄዱ (9፥10-50)
ሀ. ወደ ገሊላ ባሕር ምሥራቃዊ ዳርቻ (9፥10-17)
ለ. ወደ ፊልጶስ ቂሣርያ (9፥18-50)
6. በይሁዳ የነበረው አገልግሎት (9፥51-13፥21)
ሀ. በሰማርያ በኩል ወደ ይሁዳ ያደረገው ጉዞ (9፥51-62)
ለ. የሰባዎቹ የአገልግሎት ተልእኮ (10፥1-24)
ሐ. ስለ ሕግ ዐዋቂውና ስለ ደጉ ሳምራዊ የተነገረው ምሳሌ (10፥25-37)
መ. በቢታንያ ከማርያምና ከማርታ ጋር (10፥38-42)
ሠ. በይሁዳ ማስተማሩ (11፥1-13፥21)
7. በፔርያና በአካባቢው የነበረው አገልግሎቱ (13፥22-19፥27)
ሀ. ጠባቡ በር (13፥22-30)
ለ. ከሄሮድስ ስለ መጠንቀቅ (13፥31-35)
ሐ. በአንድ ፈሪሳዊ ቤት (14፥1-23)
መ. ደቀ መዝሙርነት የሚያስከፍለው ዋጋ (14፥24-35)
ሠ. ስለጠፋው በግ፣ ስለ ጠፋው ሳንቲምና ስለ ጠፋው ልጅ ምሳሌ (ምዕ 15)
ረ. ስለ ብልኀ መጋቢ ምሳሌ (16፥1-18)
ሰ. ሀብታሙ ሰውና አልዓዛር (16፥19-31)
ሸ. ልዩ ልዩ ትምህርቶች (17፥1-10)
ቀ. ከለምጽ የተፈወሱ ዐሥር ሰዎች (17፥11-19)
በ . የእግዚአብሔር መንግሥት መምጣት (17፥20-37)
ተ. ትጉዋ መበለት (18፥1-18)
ቸ. ፈሪሳዊውና ቀረጥ ሰብሳቢው (18፥9-14)
ኀ. ኢየሱስና ሕፃናት (18፥15-17)
ነ. ወጣቱ ሀብታም (18፥18-30)
ኘ. ክርስቶስ ስለ መሞቱ አስቀድሞ መናገሩ (18፥31-34)
አ. የዐይነ ስውሩ ለማኝ ዐይን መብራት (18፥35-43)
ከ. ኢየሱስና ዘኬዎስ (19፥1-10)
ወ. ስለ ዐሥሩ ምናን ምሳሌ (19፥11-27)
8. የመጨረሻዎቹ ቀናት፤ መከራና ድል (19፥28-24፥53)
ሀ. በክብር ወደ ኢየሩሳሌም መግባቱ (19፥28-44)
ለ. ቤተ መቅደስን ማንጻቱ (19፥45-48)
ሐ. ከአይሁድ አለቆች ጋር የነበረው የመጨረሻ ክርክር (ምዕ 20)
መ. በደብረ ዘይት ተራራ ላይ የሰጠው ገለጻ (ምዕ 21)
ሠ. የመጨረሻው እራት (22፥1-38)
ረ. ኢየሱስ በጌቴሴማኒ መጸለዩ (22፥39-46)
ሰ. የኢየሱስ መያዝ (22፥47-65)
ሸ. ኢየሱስ ለፍርድ መቅረቡ (22፥66-23፥25)
ቀ. ስቅለት (23፥26-56)
በ. ትንሣኤ (24፥1-12)
ተ. ከትንሣኤው በኋላ ማገልገሉ (24፥13-49)
ቸ. ዕርገቱ (24፥50-53)

## መግቢያ

1፥1-4 ማመ ሐሥ 1፥1

**1** በእኛ መካከል ስለ ተፈጸሙት[1] ነገሮች ብዙዎች ታሪኩን የተቻላቸውን ያህል ጽፈውት ይገኛል፤ [2]ይህም ታሪክ ከመጀመሪያው አንሥቶ የዐይን ምስክሮችና የቃሉ አገልጋዮች የነበሩት ያስተላለፉልን ነው። [3]ክቡር ቴዎፍሎስ ሆይ፤ እኔም በበኩሌ ሁሉን ከመሠረቱ በጥንቃቄ ከመረመርሁ በኋላ፣ ታሪኩን ቅደም ተከተሉን በጠበቀ ሁኔታ ልጽፍልህ መልካም ሆኖ ታየኝ፤ [4]ይህንንም የማደርገው የተማርኸው ነገር እውነተኛ መሆኑን እንድታውቅ ነው።

## የመጥምቁ ዮሐንስ መወለድ አስቀድሞ ተነገረ

[5]በይሁዳ ንጉሥ በሄሮድስ ዘመን፣ ከአብያ የክህነት ምድብ የሆነ ዘካርያስ የሚባል አንድ ካህን ነበረ፤ ሚስቱ ኤልሳቤጥም ከአሮን ነገድ ነበረች። [6]ሁለቱም የጌታን ትእዛዝና ሥርዐት ሁሉ ጠብቀው ያለ ነቀፋ የሚኖሩ፣ በእግዚአብሔር ፊት ጻድቃን ነበሩ፤ [7]ይሁን እንጂ ኤልሳቤጥ መካን በመሆኗ ልጅ አልነበራቸውም፤ ሁለቱም በዕድሜ የገፉ ነበሩ።

[8]አንድ ቀን ዘካርያስ በምድቡ ተራ፣ በእግዚአብሔር ፊት በክህነት በሚያገለግልበት ጊዜ፣ [9]በሥርዐተ ክህነቱ መሠረት፣ ወደ ጌታ ቤተ መቅደስ ገብቶ ለማጠን በዕጣ ተመረጠ። [10]ዕጣን በሚታጠንበትም ጊዜ ሕዝቡ ሁሉ በውጭ ሆኖ ይጸልይ ነበር።

[11]የጌታም መልአክ ከዕጣን መሠዊያው በስተ ቀኝ ቆሞ ታየው። [12]ዘካርያስም ባየው ጊዜ ደነገጠ፤ በፍርሀትም ተዋጠ። [13]መልአኩ ግን እንዲህ አለው፤ "ዘካርያስ ሆይ፤ አትፍራ፤ ጸሎትህ ተሰምቶአል፤ ሚስትህ ኤልሳቤጥ ወንድ ልጅ ትወልድልሃለች፤ ስሙንም ዮሐንስ ትለዋለህ። [14]በእርሱ ተድላና ደስታ ታገኛለህ፤ ብዙዎችም እርሱ በመወለዱ ደስ ይላቸዋል፤ [15]በጌታ ፊት ታላቅ ይሆናልና። የወይን ጠጅም ሆነ ሌላ የሚያሰክር መጠጥ አይጠጣም፤ በእናቱም ማሕፀን ሳለ በመንፈስ ቅዱስ ይሞላል። [16]ከእስራኤልም ሰዎች ብዙዎቹን ወደ ጌታ ወደ አምላካቸው ይመልሳቸዋል፤ [17]የአባቶችን ልብ ወደ ልጆቻቸው፣ የማይታዘዙትንም ወደ ጻድቃን ጥበብ ይመልስ ዘንድ፣ ለጌታ የተገባ ሕዝብ ለማዘጋጀት በኤልያስ መንፈስና ኀይል በጌታ ፊት ይሄዳል።"

1፥2 ማር1፥1፤4፥14፤ሐሥ1፥21፡22፤ዕብ2፥3፤1ጴጥ5፥1፤2ጴጥ1፥16፤1ዮሐ1፥1
1፥3 ሐሥ1፥1፤11፥4፤24፥3፤26፥25
1፥4 ዮሐ20፥31፤ሐሥ2፥42
1፥5 1ዜና24፥10፤ማቴ2፥1
1፥6 ዘፍ6፥9፤ዘዳ5፥33፤1ነገ9፥4፤ሉቃ2፥25
1፥8 1ዜና24፥19፤2ዜና8፥14
1፥9 ዘፀ30፥7፡8፤1ዜና23፥13፤2ዜና29፥11፤መዝ141፥2፤ሐሥ 1፥26
1፥10 ዘሌ16፥17
1፥11 ዘፀ30፥1-10፤ሐሥ5፥19
1፥12 መሳ6፥22፡23፤13፥22
1፥13 ቍ30፤60፡63፤ማቴ3፥1፤14፥27
1፥14 ቍ58
1፥15 ቍ41፡67፤ዘሌ 10፥9፤ዘኍ6፥3፤መሳ13፥4፤ኤር1፥5፤ሉቃ7፥33፤ሐሥ2፥4፤4፥8፡31፤6፥3፡5፤9፥17፤10፥44፤ገላ1፥15፤ኤፌ5፥18
1፥17 ቍ76፤ሚል4፥5፡6፤ማቴ3፥3፤11፥14

[1] *በእርግጥ ስለታመኑት*

*1፥1-4፤* ሉቃስ ከጥንቱ የግሪክ ቋንቋ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ቋንቋ በመጠቀም፣ በዚያን ዘመን እንደ ነበሩት የታሪክ ጸሐፊዎች፣ ይህን ወንጌል የጻፈበትን ዐላማና ለማን እንደ ጻፈ ለመግለጽ ጽሑፉን የጀመረው መቅድም በመጻፍ ነው። ሌሎች ጸሐፊዎች በዚሁ ጕዳይ ላይ እንደ ተጻፉ አመልክቶ፣ የዚህን አዲስ ጽሑፍ አስፈላጊነት፣ የአጻጻፉን ስልትና የመረጃ ምንጩ ከየት እንደ ሆነ ገልጾአል።

1፥1 *በእኛ መካከል ስለ ተፈጸሙት ነገሮች፤* በብሉይ ኪዳን ተነግረው የነበሩት ትንቢቶችና አሁን ሙሉ በሙሉ የተፈጸሙትን የሚያመለክት ነው።

1፥2 *የዐይን ምስክሮችና የቃሉ አገልጋዮች የነበሩት ያስተላለፉልን፤* በዚያን ዘመን ተቀባይነት የነበረውን፣ መረጃ የማስተላለፍ ልማድ የሚያመለክት አባባል ነው። ሉቃስ ራሱ የዐይን ምስክር ባይሆንም፣ ወንጌልን በማሰራጨት ትጕሐን ከነበሩት የዐይን ምስክሮች ምስክርነት ተቀብሏል። የሐዋርያትን ስብከት ለመስማትና የኢየሱስ አገልግሎት የዐይን ምስክሮች ከነበሩት ቃለ መጠይቅ በማቅረብ የሚፈልገውን መረጃ ለማግኘት አመቺ ሁኔታ ነበረው።

1፥3 *ክቡር፤* ጳውሎስ፣ ይህን የማዕረግ ስም ገዢዎች የነበሩትን ፊልክስንና (ሐሥ24፥3) ፊስጦስን (ሐሥ 26፥25) ለመጥራት ተጠቅሞበታል። *ቴዎፍሎስ፤* በመግቢያው ላይ "የመልእክቱ ተደራሲያንና ዐላማ" በሚል ንዑስ ርእስ ሥር የተጻፈውን ይመ። *በጥንቃቄ ከመረመርሁ በኋላ፤* በማንኛውም ረገድ ተመዝኖ የቀረበ በመሆኑ፣ ሉቃስ የጻፈው እያንዳንዱ ታሪካዊ ዘገባ ትክክል ነበር። በመንፈስ ቅዱስ መመራት፣ የሰውን ቀና የሆነ ጥረት አስፈላጊነት አይቃወምም። ኢየሱስ በምድር የኖረውን ሕይወት ከመጀመሪያ አንሥቶ ስለሚተርክ የተሟላ ነው። አተራረኩም ቅደም ተከተልን የጠበቀ፣ ሥርዐት ያለውና ትርጕም በሚሰጥ ሁኔታ የተቀናጀ ነበር።

1፥4 *እንድታውቅ፤* ሐዋርያው ዮሐንስ ወንጌሉን ከጻፈበት ዓላማ ጋር ያነጻጽሩ (ዮሐ 20፥31)።

1፥5 *በይሁዳ ንጉሥ በሄሮድስ፤* ታላቁ ሄሮድስ ከ37-4 ዓ.ቅ.ክ. ድረስ የነገሠና ግዛቱም ሰማርያን፣ ገሊላን፣ አብዛኛውን የፔሪያን ምድርና የኮሌ ሶርያን ክፍልን የሚሸፍን ነበር (የማቴ 2፥1 ማብ ይመ)፣ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ዘመን ከ7-6 ዓ.ቅ.ክ ያለውን የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም። *ዘካርያስ... ኤልሳቤጥ፤* ሁለቱም ከአሮን የዘር ሐረግ የሆኑና የካህናት ወገኖች ናቸው። *ከአብያ የክህነት ምድብ፤* ከዳዊት ዘመን ጀምሮ፣ ካህናቱ በ24 ክፍሎች ተመድበው ነበር፤ አብያም "ከካህናት ቤተ ሰብ አለቆች" አንዱ ነበር (ነህ 12፥12፤ 1ዜና 24፥10 ይመ)።

1፥6 *ያለ ነቀፋ... ጻድቃን፤* ኀጢአት ሠርተው አያውቁም ማለት አይደለም፤ ነገር ግን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ለማክበር፣ ታማኞችና ቅኖች ነበሩ ማለት ነው። ስምዖንና (2፥25) ዮሴፍም (ማቴ 1፥19) ይህን ዐይነት ምሥጋና አግኝተዋል። በተመሳሳይ ሁኔታ ተመስግነዋል።

1፥7 **ልጅ አልነበራቸውም** የቍ 25 ማብ ይመ።

1፥9፤ ከካህናት ተግባራት አንዱ፣ በቅድስተ ቅዱሳን ፊት ለፊት ባለው መሠዊያ ላይ ዕጣን ማጠን ነበር። ስለዚህም ከማለዳው መሥዋዕት በፊትና ከሠርክ መሥዋዕት በኋላ፣ በመሠዊያው ላይ አዲስ ዕጣን ይጨምር ነበር (ዘፀ 30፥6-8)። በመሠረቱ አንድ ካህን እንደዚህ ያለ ዕድል ብዙ ጊዜ አያጋጥመውም ነበር፤ እንዲያውም አንዳንድ ካህናትን ዕድሉ ጭራሽ ላያጋጥማቸው ይችላል፤ ምክንያቱም የሥራ ድልድል የሚደረገው በዕጣ ስለ ነበር ነው። *በዕጣ ተመረጠ፤* የነህ 11፥1፤ ምሳ 16፥33፤ ዮና 1፥7 ሐሥ 1፥26 ማብ ይመ።

1፥11 *የጌታም መልአክ፤* ቍ 19 ይመ። ከዕጣን መሠዊያው በስተ ቀኝ፤ የመሠዊያው ፊት ወደ ምሥራቅ ስለ ነበር፣ መልአኩ የቆመው በደቡብ በኩል ነበር።

1፥12 *ፍርሀት፤* በጌዴዎንና (መሳ 6፥22-23) በማኑሄ (13፥22) የታየው ዐይነት ማለት ነው።

1፥13 *አትፍራ፤* በብሉይና በአዲስ ኪዳን እንዲህ ዐይነቱ የማበረታቻ ቃል ብዙ ጊዜ ተሰጥቷል (ለምሳሌ ቍ 30፤ 2፥10 እና ማብ 5፥10፤ 8፥50፤ 12፥7፡ 32፤ ዘፍ 15፥1፤ 21፥17፤ 26፥24፤ ዘዳ 1፥21፤ ኢሱ 8፥1፡ ይመ)። *ዮሐንስ፤* ይህ ስም ከዕብራይስጥ ቋንቋ የተወሰደ ሲሆን፣ ትርጕሙም "እግዚአብሔር ባለ ጸጋ ነው" ማለት ነው።

1፥14 *ደስታ፤* ለዚህ ወንጌል የመጀመሪያው ምዕራፎች ቍልፍ ቃል ነው። (ቍ 14፡44፡47፡58፤ 2፥10)።

1፥15 *የወይን ጠጅም ሆነ ሌላ የሚያሰክር መጠጥ፤* የሚያሰክር መጠጥ ሳለመጠጣት፣ ዮሐንስ በናዝራዊ መሐላ ውስጥ የገባ ይመስላል (ዘኍ 6፥1-4)፤ እንዲህ ከሆነ ደግሞ እንደ ሳምሶንና (መሳ 13፥4-7) ሳሙኤል (1ሳሙ 1፥11) የዕድሜ ልክ ናዝራዊ ሆኖአል ማለት ነው።

1፥17 *የአባቶችን ልብ ወደ ልጆቻቸው... ይመልስ ዘንድ፤* የሚል 4፥6 ማብ ይመ። *ለጌታ የተገባ ሕዝብ፤* በሉቃ 3፥4-6 እንደተጠቀሰው፣ መጥምቁ ዮሐንስ በኢሳይያስ የተነገረው ትንቢት ፍጻሜ ነበር (ኢሳ 40፥3-5)። *ኤልያስ፤* ዮሐንስ፣ ዳግም ሥጋ ለብሶ ወደ ምድር የተመለሰ ኤልያስ አልነበረም (ዮሐ 1፥21)፤ ይሁን እንጂ በብሉይ ኪዳን የንስሓ ስብከት እንደ ሰበከው እንደ ኤልያስ በማገልገሉ፣ በሚል 4፥5-6 የተነገረው ትንቢት መፈጸሙን ያሳያል (ማቴ 11፥14፤ 17፥10-13 ይመ)።

18ዘካርያስም መልአኩን፣ "ይህን በምን አውቃለሁ? እኔ ሽማግሌ ነኝ፤ ሚስቴም በዕድሜ ገፍታለች" አለው።

19መልአኩም መልሶ እንዲህ አለው፤ "እኔ በእግዚአብሔር ፊት የምቆመው ገብርኤል ነኝ፤ ይህን እንድነግርህና ይህን የምሥራች አመጣልህ ዘንድ ተልኬአለሁ፤ 20እነሆ፤ ጊዜውን ጠብቆ የሚፈጸመውን ቃሌን ስላላመንህ፣ ድዳ ትሆናለህ፤ መናገርም አትችልም።"

21በዚህ ጊዜ ሕዝቡ ዘካርያስ ከቤተ መቅደሱ ሳይወጣ ለምን እንደ ዘገየ በመገረም ይጠባበቅ ነበር። 22ከወጣ በኋላም ሊያናግራቸው አልቻለም፤ በምልክት ከመጥቀስ በስተቀር መናገር ባለመቻሉ በቤተ መቅደስ ውስጥ ራእይ እንዳየ ተገነዘቡ።

23ዘካርያስም የአገልግሎቱ ወቅት በተፈጸመ ጊዜ ወደ ቤቱ ተመለሰ። 24ከዚህ በኋላ ሚስቱ ኤልሳቤጥ ፀነሰች፤ አምስት ወራትም ራሷን ሰወረች፤ 25እርሷም፣ "ጌታ በምሕረቱ ነቀፌታዬን ከሰው መካከል ሊያስወግድልኝ ተመልክቶ በዚህ ጊዜ ይህን አድርጎልኛል" አለች።

## የኢየሱስ መወለድ አስቀድሞ ተነገረ

26በስድስተኛው ወር፣ እግዚአብሔር መልአኩ ገብርኤልን በገሊላ ወደምትገኘው ወደ ናዝሬት ከተማ ላከው፤ 27የተላከውም ከዳዊት ዘር ለሆነ ዮሴፍ ለሚባል ሰው ወደ ታጨች ወደ አንዲት ድንግል ነበር፤ የድንግሊቱም ስም ማርያም ነበረ። 28መልአኩም እርሷ ወዳለችበት ገብቶ፣ "እጅግ የተወደድሽ ሆይ፤ ሰላም ለአንቺ ይሁን፤ ጌታ ከአንቺ ጋር ነው፤ አንቺ የተባረክሽ ነሽ" አላት።

29ማርያምም በንግግሩ እጅግ በጣም ግጣ፣ "ይህ ምን ዐይነት ሰላምታ ይሆን?" እያለች ነገሩን ታሰላስል ጀመር፤ 30መልአኩም እንዲህ አላት፤ "ማርያም ሆይ፤ በእግዚአብሔር ዘንድ ሞገስ አግኝተሻልና አትፍሪ። 31እነሆ፤ ትፀንሻለሽ፤ ወንድ ልጅም ትወልጃለሽ፤ ስሙንም ኢየሱስ ትዪዋለሽ። 32እርሱም ታላቅ ይሆናል፤ የልዑል ልጅም ይባላል፤ ጌታ አምላክ የአባቱን የዳዊትን ዙፋን ይሰጠዋል፤ 33በያዕቆብም ቤት ላይ ለዘላለም ይነግሣል፤ ለመንግሥቱም ፍጻሜ የለውም።"

34ማርያምም መልአኩን፣ "እኔ ወንድ ስለማላውቅ ይህ እንዴት ሊሆን ይችላል?" አለችው።

35መልአኩም መልሶ እንዲህ አላት፤ "መንፈስ ቅዱስ በአንቺ ላይ ይመጣል፤ የልዑልም ኀይል ይጸልልሻል፤ ስለዚህ የሚወለደው ቅዱሱ ሕፃን፣ የእግዚአብሔር ልጅ ይባላል። 36እነሆ፤ ዘመድሽ ኤልሳቤጥም በስተ እርጅናዋ ወንድ ልጅ ፀንሳለች፤ መካን የተባለችውም ስድስተኛ ወሯን ይዛለች፤ 37ለእግዚአብሔር የሚሳነው ነገር የለምና።"

38ማርያምም፣ "እነሆ፤ እኔ የጌታ ባሪያ ነኝ፤ እንደ ቃልህ ይሁንልኝ" አለች። ከዚያም መልአኩ ተለይቶአት ሄደ።

## ማርያም ኤልሳቤጥን ጥየቃ ሄደች

39ማርያምም በዚያው ሰሞን በፍጥነት ተነሥታ ወደ ደጋው አገር፣ ወደ አንድ የይሁዳ ከተማ ሄደች፤ 40ወደ ዘካርያስ ቤትም ገብታ ለኤልሳቤጥ ሰላምታ አቀረበች። 41ኤልሳቤጥም የማርያምን ሰላምታ በሰማች ጊዜ፣ ፅንሱ በማሕፀኗ ውስጥ ዘለለ፤ ኤልሳቤጥም በመንፈስ ቅዱስ ተሞላች፤ 42ድምፅዋን ከፍ

1፥18 ቍ34፤ ዘፍ15፥8፤17፥17
1፥19 ቍ26፤ ዳን8፥16፤9፥21
1፥20 ዘፀ4፥11፤ ሕዝ3፥26
1፥22 ቍ62
1፥25 ዘፍ30፥23፤ ኢሳ 4፥1
1፥26 ቍ19፤ ማቴ2፥23
1፥27 ማቴ1፥16፡ 18፡20፤ሉቃ2፥4
1፥30 ቍ13፤ዘፍ 6፥8፤ማቴ14፥27
1፥31 ኢሳ7፥14፤ ማቴ1፥21፡25፤ ሉቃ2፥21
1፥32 ቍ35፡76፤ ማቴ1፥1፤ማር 5፥7
1፥33 2ሳሙ7፥16፤ መዝ89፥3-4፤ ኤር33፥17፤ዳን2፥44፤ 7፥14፤ኢሳ 9፥7፤ 27፤ሚክ4፥7፤ ማቴ28፥18፤ዕብ1፥8
1፥35 ቍ32፡76፤ ማቴ1፥18፤ 4፥3፤ ማር1፥24፤5፥7
1፥36 ቍ24
1፥37 ማቴ19፥26
1፥39 ቍ65
1፥41 ቍ15

1፥18 *በምን አውቃለሁ?* እንደ አብርሃም (ዘፍ 15፥8)፣ ጌዴዎንና (መሳ 6፥17) ሕዝቅያስ (2ነገ 20፥8)፣ ዘካርያስም ምልክት ጠየቀ (ከ1ቆሮ 1፥22 ጋር ያነጻጽሩ)።

1፥19 *ገብርኤል፤* የዚህ ስም ትርጒም፣ "እግዚአብሔር የእኔ ጀግና ነው" ወይም "የእግዚአብሔር ኀያል ሰው" ማለት ነው። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ፣ በስም የሚታወቁ መላእክት ሁለት ብቻ ናቸው፤ እነርሱም፣ ገብርኤልና (ዳን 8፥16፤ 9፥21) ሚካኤል ናቸው (ዳን 10፥13፡ 21፤ ይሁ 9፤ ራእ 12፥7)።

1፥21 *ሕዝቡ ዘካርያስ... ይጠባበቅ ነበር፤* ከመቅደስ ወጥቶ የአሮንን ቡራኬ እንዲያሰማቸው ይጠባበቁ ነበር (ዘኍ 6፥24-26)።

1፥23 *የአገልግሎቱ ወቅት፤* እያንዳንዱ ካህን፣ በየስድስት ወሩ አንድ ጊዜ ለአንድ ሳምንት ሙሉ በቤተ መቅደስ የማገልገል ኀላፊነት ነበረበት። *ቤቱ፤* ቍ 39 ይመ።

1፥24 *ሰወረች፤* እግዚአብሔር የመካንነትን የሕይወት ታሪኳን ስለ ለወጠላት በደስታ፣ በጥሞናና ምስጋና ለማቅረብ ነበር።

1፥25 *ጌታ በምሕረቱ ነቀፌታዬን... ሊያስወግድልኝ፤* ልጅ አለመውለድ፣ የወላጆችን የግል ደስታ የሚያሳጣ ብቻ ሳይሆን፣ እግዚአብሔር እንደማይወዳቸው የሚያመላክት ነው ተብሎ ስለሚታመን፣ በኅብረተ ሰቡ ዘንድ ነቀፌታን የሚያስከትል ነበር (በዘፍ 16፥2 *ሦራን*፣ በ25፥21 *ርብቃን*፣ በ30፥23 *ራሔልን*፣ በ1ሳሙ 1፥1-18 *ሐናን*፣ ይመ፤ እንዲሁም ዘሌ 20፥20-21፤ መዝ 128፥3፤ ኤር 22፥30 ይመ)።

*1፥26-35፤* ይህ ክፍል፣ ኢየሱስ ከድንግል እንደ ተፀነሰ ይናገራል (ቍ27፡34-35፤ ማቴ 1፥18-25 ይመ)፤ ኢየሱስ የተፀነሰው በመንፈስ ቅዱስ ነው፤ ከሥላሴ ሁለተኛው፣ አካል ዘላለማዊ አምላክ ሆኖ ሳለ፣ "ሥጋ ሆነ" (ዮሐ 1፥14)። ኢየሱስ ከመፀነሱ ጀምሮ ፍጹም አምላክና ፍጹም ሰው ነበር።

1፥26 *በስድስተኛው ወር፤* ዮሐንስ ከተፀነሰበት ጊዜ ጀምሮ ማለት ነው። *ናዝሬት፤* የማቴ 2፥23 ማብ ይመ።

1፥27 *ወደ ታጨች፤* የማቴ 1፥18 ማብ ይመ።

1፥31 *ኢየሱስ፤* የዚህን ስም ትርጒም በተመለከተ፣ የማቴ 1፥21 አማራጭ ትርጒም ይመ።

1፥32 *የልዑል ልጅ፤* ይህ የማዕረግ ስም ሁለት ነገሮችን ያመለክታል፤ እነዚህንም፣ (1) የእግዚአብሔር የመለኮት ልጅ መሆኑንና (2) ጊዜው ሲደርስ የተወለደ መሲሕ መሆኑን ነው። መሲሕነቱ በግልጽ የተመለከተው ቀጥሎ ባለው ዐውደ ምንባብ ላይ ነው (ቍ 32-33)። *ልዑል፤* በብሉይና በአዲስ ኪዳን ብዙውን ጊዜ ለእግዚአብሔር የተሰጠ የማዕረግ ስም ነው (ቍ 35፡76፤ 6፥35፤ 8፥28፤ ዘፍ 14፥19 እና ማብ፤ 2ሳሙ 22፥14፤ መዝ 7፥10 ይመ)። ከዳዊት ዘር ለሆነው መሲሕ በብሉይ ኪዳን የተገባ ተስፋ ነው (2ሳሙ 7፥13፡16፤ መዝ 2፥6-7፤ 89፥26-27፤ ኢሳ 9፥6-7)። ዮሴፍ ከዳዊት ዘር እንደ ሆነ ሁሉ፣ ማርያምም ከዳዊት ዘር ናት (ማቴ 1፥16 ይመ)፤ ስለዚህ ኢየሱስ የዳዊት "ልጅ" ተብሎ ሊጠራ ይገባዋል።

1፥33 *ለዘላለም፤* መዝ 45፥6፤ ራእ 11፥15 ይመ። *ለመንግሥቱም ፍጻሜ የለውም፤* የክርስቶስ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል መሆን አንድ ቀን የሚያበቃ ቢሆንም (1ቆሮ 15፥24-28 ይመ)፣ አብና ወልድ በአንድነት የሚገዙበት መንግሥት ግን ፍጻሜ የለውም።

1፥34 *ይህ እንዴት ሊሆን ይችላል?* ማርያም የጠየቀችው እንደ ዘካርያስ (ቍ 20)፣ ባለማመን አልነበረም (ቍ 45 ይመ)።

1፥35 *ቅዱሱ፤* ኢየሱስ ከቶ ኀጢአት አላደረገም (2ቆሮ 5፥21፤ ዕብ 4፥15፤ 7፥26፤ 1ጴጥ 2፥22፤ 1ዮሐ 3፥5)።

1፥36 *ዘመድሽ ኤልሳቤጥ፤* ዝምድናቸው ምን ዐይነት እንደ ሆነ አይታወቅም።

አድርጋ እንዲህ አለች፤ "አንቺ ከሴቶች መካከል የተባረክሽ ነሽ፤ የማሕፀንሽም ፍሬ የተባረከ ነው:: [43]ለመሆኑ የጌታዬ እናት ወደ እኔ ትመጣ ዘንድ እኔ ማን ነኝ? [44]እነሆ፤ የሰላምታሽ ድምፅ ጆሮዬ እንደ ገባ፣ በማሕፀኔ ያለው ፅንስ በደስታ ዘሎ አለና:: [45]ጌታ ይፈጸማል ብሎ የነገራትን ያመነች እርሷ የተባረከች ናት!"

## የማርያም መዝሙር

1፥46-53 ተጓ ምብ – 1 ሳሙ 2፥1-10

[46]ማርያምም እንዲህ አለች፤

"ነፍሴ ጌታን ከፍ ከፍ ታደርገዋለች፤
[47]መንፈሴም በመድኀኒቴ
በእግዚአብሔር ደስ ትሰኛለች፤
[48]እርሱ የባሪያውን መዋረድ
ተመልክቶአልና::
ከዛሬ ጀምሮ ትውልድ ሁሉ
ብፅዕት ይሉኛል፤
[49]ኀያል የሆነው እርሱ ታላቅ
ነገር አድርጎልኛልና፤
ስሙም ቅዱስ ነው፤
[50]ምሕረቱም ለሚፈሩት ከትውልድ
እስከ ትውልድ ይኖራል::
[51]በክንዱ ብርቱ ሥራ ሠርቶአል፤
በልባቸው ሐሳብ የሚታበዩትን
በትኖአቸዋል፤
[52]ገዦችን ከዙፋናቸው አውርዶአቸዋል፤
ትሑታንን ግን ከፍ ከፍ አድርጎአቸዋል፤
[53]የተራቡትን በበጎ ነገር አጥግቦአቸዋል፤
ሀብታሞችን ግን ባዶአቸውን
ሰዶአቸዋል፤
[54]ምሕረቱን በማስታወስ፣ ባሪያውን
እስራኤልን ረድቶአል፤
[55]ይህም ለአባቶቻችን እንደ ተናገረ፣
ለአብርሃምና ለዘሩ ያለውን
ለዘላለም ለመጠበቅ ነው::"

[56]ማርያምም ሦስት ወር ያህል ኤልሳቤጥ ዘንድ ከቈየች በኋላ ወደ ቤቷ ተመለሰች::

1፥42 መሳ5፥24
1፥43 ዮሐ13፥13
1፥46 መዝ34፥2፡3
1፥47 መዝ18፥46፤ ኢሳ17፥10፤61፥10፤ ዕን3፥18፤1ጢሞ 1፥1፤2፥3፤4፥10
1፥48 ቊ38፤መዝ 138፥6፤ሉቃ11፥27
1፥49 መዝ71፥19፤ 111፥19
1፥50 ዘፀ20፥6፤ መዝ103፥17
1፥51 ዘፍ11፥8፤ዘፀ 18፥11፤2ሳሙ22፥28 ፤መዝ98፥1፤ኢሳ 40፥10፤ኤር13፥9፤ 49፥16
1፥52 ማቴ23፥12
1፥53 መዝ107፥9
1፥54 መዝ98፥3
1፥55 ገላ3፥16
1፥59 ዘፍ17፥12፤ ዘሌ12፥3፤ሉቃ2፥21፤ ፊል3፥5
1፥60 ቊ13፡63፤ ማቴ3፥1
1፥62 ቊ22
1፥63 ቊ13፡60፤ ማቴ3፥1
1፥64 ቊ20፤ ሕዝ24፥27
1፥65 ቊ39
1፥66 ዘፍ39፥2፤ ሐሥ11፥21
1፥67 ቊ15፤ ኢል2፥28
1፥68 ዘፍ24፥27፤ 1ነገ8፥15፤መዝ72፥ 18፤111፥9፤ሉቃ7፥16
1፥69 1ሳሙ2፥1፡ 10፤2ሳሙ22፥3፤ መዝ18፥2፤89፥17 ፤132፥17፤ሕዝ 29፥21፤ማቴ1፥1
1፥70 ኤር23፥5፤ ሐሥ3፥21፤ ሮሜ1፥2፤
1፥72 መዝ105፥8፡ 9፤106፥45፤ሕዝ 16፥60፤ሚክ7፥20

## የመጥምቁ የዮሐንስ መወለድ

[57]የኤልሳቤጥም የመውለጃዋ ቀን ደረሰ፤ ወንድ ልጅም ወለደች:: [58]ጎረቤቶቿና ዘመዶቿም ጌታ ታላቅ ምሕረት እንዳደረገላት ሰሙ፤ የደስታዋም ተካፋዮች ሆኑ::

[59]በስምንተኛውም ቀን ሕፃኑን ሊገርዙት መጡ፤ በአባቱም ስም ዘካርያስ ሊሉት ፈለጉ፤ [60]እናቱ ግን፣ "አይሆንም፤ ዮሐንስ መባል አለበት" አለች::

[61]እነርሱም፣ "ከዘመዶችሽ በዚህ ስም የተጠራ ማንም የለም" አሏት::

[62]አባቱንም ምን ስም ሊያወጣለት እንደ ሚፈልግ በምልክት ጠየቁት:: [63]እርሱም መጻፊያ ሰሌዳ እንዲሰጡት ለምኖ፣ "ስሙ ዮሐንስ ነው" ብሎ ጻፈ፤ ሁሉም በነገሩ ተደነቁ:: [64]ወዲያውም አፉ ተከፈተ፤ አንደበቱ ተፈታ፤ እግዚአብሔርንም እያመሰገነ መናገር ጀመረ:: [65]ጎረቤቶቹም ሁሉ በፍርሀት ተሞሉ፤ ይህም ሁሉ ነገር በደጋማው የይሁዳ ምድር ሁሉ ተወራ:: [66]ይህንም የሰሙ ሁሉ፣ "ይህ ሕፃን ምን ሊሆን ይሆን?" እያሉ ነገሩን በልባቸው ያዙ፤ የጌታ እጅ በእርግጥ ከእርሱ ጋር ነበርና::

## የዘካርያስ ትንቢት

[67]የሕፃኑም አባት ዘካርያስ በመንፈስ ቅዱስ ተሞልቶ እንዲህ ሲል ትንቢት ተናገረ፤

[68]"የእስራኤል አምላክ፣ ጌታ ይመስገን፤
መጥቶ ሕዝቡን ተቤዥቶአልና::
[69]በባሪያው በዳዊት ቤት፣
የድነት ቀንድ[a] አስነሥቶልናል፤
[70]ይህም ጥንት በቅዱሳን ነቢያቱ አፍ
እንደ ተናገረው፣
[71]ማዳኑም ከጠላቶቻችንና፣ ከተፃራሪዎቻችን
ሁሉ እጅ ነው፤
[72]ይህንም ያደረገው ለአባቶቻችን
ምሕረቱን ለማሳየት፣
ቅዱስ ኪዳኑን ለማስታወስ፣

[a]69 ቀንድ በዚህ ስፍራ ብርታትን በትእምርትነት ያሳያል

1፥44 *በደስታ፤* በማሕፀን ውስጥ ያለው ሕፃን፣ ሊመረመር በማይቻል ሁኔታ በደስታ እንዲዘል መንፈስ ቅዱስ አደረገ::

*1፥46-55፤* በሉቃስ ወንጌል በምዕራፍ 1 እና 2 ላይ ከሚገኙት አራት መዝሙሮች አንዱ ይህ ነው፤ (ቊ 68-79፤ 2፥29-32 እና ማብ ይመ) ይህ የምስጋና መዝሙር፣ "መወደስ" በመባል የሚታወቅ ነው፤ ከዳዊትና ከሐና መዝሙርም ጋር የሚመሳሰልና የሚነጻጸር ነው (1ሳሙ 2፥1-10፤ የ2ሳሙ 2፥1 ማብ ይመ)::

1፥50 *ለሚፈሩት፤* እግዚአብሔርን በማክበር እንደ ፈቃዱ የሚኖሩትን ማለት ነው::

1፥51 *በክንዱ፤* የእግዚአብሔርን ኀያል ሥራ በዘይቤአዊ አገላለጽ የሚያሳይ ነው:: ሆኖም ግን፣ እግዚአብሔር መንፈስ በመሆኑ፣ ሥጋዊ አካል የለውም (ዮሐ 4፥24)::

1፥53 *የተራቡትን፤* በሥጋዊና በመንፈሳዊ ራብ ያሉትን ማለት ነው (ማቴ 5፥6፤ ዮሐ 6፥35):: የእግዚአብሔር መንግሥት መምጣት በየትኛውም ዐይነት የሕይወት አቅጣጫ ለውጥ ያመጣል::

1፥54 *ምሕረቱን በማስታወስ፤* የዝማሬው መደምደሚያ፣ እግዚአብሔር ለሕዝቡ የገባውን ቃል እንዲሚያከብር የሚያስረግጥ ነው (ዘፍ 22፥16-18 ይመ)::

1፥56 *ሦስት ወር፤* ማርያም ከኤልሳቤጥ ጋር የቈየችው ዮሐንስ እስከ ተወለደበት ጊዜ ድረስ ነበር፤ ከዚያ በኋላ ግን፣ ናዝሬት ወደሚገኘው ቤቷ ተመልሳለች::

1፥59 *በአባቱም ስም፤* በዮሴፍ ወልደ ኩሪዮን ጽሑፍ እንደ ተመለከተው (ሕይወቱ 1)፣ በዚያ ዘመን ይህ ዐይነት ልማድ ነበር::

1፥62 *አባቱንም... በምልክት ጠየቁት፤* መናገር ካልቻለ፣ ሊሰማ አይችልም ከሚል ግምት የተነሣ ሊሆን ይችላል::

1፥63 *መጻፊያ ሰሌዳ፤* ስም የተቀባ አነስተኛ የዕንጨት ሰሌዳ ሊሆን ይችላል::

1፥67 *በመንፈስ ቅዱስ ተሞልቶ ... ትንቢት ተናገረ፤* ትንቢት፣ ወደፊት የሚደርሰውን የሚነገርበት ብቻ ሳይሆን፣ የእግዚአብሔርንም ቃል የሚታወጅበት ነው:: ዘካሪያስና ሚስቱም ኤልሳቤጥ (ቊ 41፡45)፣ በራሳቸው ሊናገሩ የማይችሉትን ነገር፣ በመንፈስ ቅዱስ ኀይል ለመናገር ቻሉ::

*1፥68-79፤* ይህ ዝማሬ "ቡራኬ" ተብሎ ይታወቃል፤ ምክንያቱም በዐረፍተ ነገሩ መጀመሪያ ላይ ያለው ቃል በላቲን ቅጂ ቡራኬ የሚል ስም ስላለው ነው:: "መወደስ" ከምስጋና መዝሙር ጋር ተመሳሳይ ሲሆን፣ ይህ "ቡራኬ" ግን እንደ ትንቢት ያለ ነው::

1፥68 *ሕዝቡን ተቤዥቶአልና፤* ብሔራዊ ነጻነትን ብቻ ሳይሆን (ቊ71) የሥነ ምግባርና መንፈሳዊ ድነትንም ያመለክታል (ቊ 75-77)::

1፥69 *ቀንድ፤* ኀይልን ያመለክታል (ዘዳ 33፥17፤ መዝ 22፥21፤ ሚክ 4፥13 ይመ)፤ ከዳዊት ዘር የሆነው መሲሑ ኢየሱስ፣ የማዳን ኀይል አለው (አማራጭ ትርጒም ይመ)::

73ለአባታችን ለአብርሃም የማለውን
መሐላ ለማሰብ፣
74ከጠላቶቻችን እጅ አውጥቶ፣
ያለ ፍርሀት እንድናገለግለው፣
75በዘመናችንም ሁሉ በቅድስናና
በጽድቅ በፊቱ ሊያቆመን ነው::
76ደግሞም አንተ ሕፃን ሆይ፤ የልዑል
ነቢይ ትባላለህ፤
የጌታን መንገድ ለማዘጋጀት በፊቱ
ትሄዳለህና፤
77የኀጢአታቸውን ስርየት ከማግኘታቸው
የተነሣ፤
ለሕዝቡ የመዳንን ዕውቀት ትሰጥ ዘንድ፣
78ከአምላካችንም በጎ ምሕረት የተነሣ፣
የንጋት ፀሓይ ከሰማይ ወጣችልን፤
79ይኸውም በጨለማ ለሚኖሩት፣
በሞት ጥላ ውስጥም ላሉት እንዲያበራና፣
እግሮቻችንንም ወደ ሰላም
መንገድ እንዲመራ ነው::"

80ሕፃኑም አደገ፤ በመንፈስም ጠነከረ፤ ለእስ ራኤልም ሕዝብ በይፋ እስከ ታየበት ቀን ድረስ በበረሓ ኖረ::

## የኢየሱስ መወለድ

**2** በዚያን ዘመን፣ የዓለሙ ሁሉ ሕዝብ እን ዲቈጠርና እንዲመዘገብ ከአውግስጦስ ቄሳር ትእዛዝ ወጣ:: 2ይህም ቄሬኔዎስ የሶርያ ገዢ በነበረበት ጊዜ የተደረገ የመጀመሪያው የሕዝብ ቈጠራ ነበር:: 3ስለዚህ እያንዳንዱ ሰው ለመመዝገብ ወደየራሱ ከተማ ሄደ::

4ዮሴፍም ከዳዊት ቤትና ወገን ስለ ነበረ፣ በገሊላ አውራጃ ከምትገኘው ከናዝሬት ከተማ ተነሥቶ የዳዊት ከተማ ወደሆነችው፣ ቤተ ልሔም ወደምትባል ከተማ ወደ ይሁዳ ወጣ:: 5ወደዚያም ለመመዝገብ የተጓዘው፣ የመው ለጃ ጊዜዋ ከተቃረበው ከእጮኛው ከማር ያም ጋር ነበር:: 6በዚያም እንዳሉ የምትወ ልድበት ጊዜ ደረሰ፤ 7የበኵር ልጇ የሆነ ውን ወንድ ልጅ ወለደች፤ በጨርቅም ጠቀ ለለችው፤ በእንግዶችም ማረፊያ ቦታ ስላላ ገኙ በግርግም አስተኛችው::

## እረኞችና መላእክት

8በዚያው አገር በሌሊት መንጋቸውን ሲጠብቁ በሜዳ የሚያድሩ እረኞች ነበሩ:: 9የጌታም መልአክ ድንገት መጥቶ በአጠ ገባቸው ቆመ፤ የጌታም ክብር በዙሪያቸው አበራ፤ ታላቅም ፍርሀት ያዛቸው:: 10መል አኩ ግን እንዲህ አላቸው፤ "አትፍሩ፤ ለሕ ዝቡ ሁሉ የሚሆን ታላቅ ደስታ የምሥራች አምጥቼላችኋለሁና:: 11ዛሬ በዳዊት ከተማ መድኅን ተወልዶላችኋልና፤ እርሱም ጌታ

1፥73 ዘፍ22፥16-18
1፥74 ዕብ9፥14፤ 1ዮሐ4፥18
1፥75 ኤፌ4፥24
1፥76 ቍ17፡32፡35፤ ማቴ3፥3፤11፥9፤ ማር5፥7
1፥77 ኤር31፥34፤ ማቴ1፥21ማር1፥4
1፥78 ሚል4፥2
1፥79 መዝ 107፥14፤ ኢሳ 9፥2፤ 59፥9፤ማቴ4፥16፤ ሉቃ2፥14፤ሐሥ 26፥18
1፥80 ሉቃ2፥40:52
2፥1 ማቴ22፥17፤ 24፥14፤ሉቃ3፥1
2፥2 ማቴ4፥24፤ ሐሥ 15፥23:41፤ 21፥3፤ ገላ1፥21
2፥4 ዮሐ7፥42
2፥5 ሉቃ1፥27
2፥9 ሐሥ5፥19
2፥11 ማቴ1፥16፡ 21፥16፥16:20፤ዮሐ 3፥17፤4፥42፤11፥27፤ 3፥13፤ሐሥ2፥36፤ 3፥20፤5፥31፤9፥22፤ 13፥23፤ሮሜ1፥14፤1 ጢሞ4፥10፤ 1ዮሐ4፥14

1፥74 *እጅ አውጥቶ፤* ከማንኛውም ዐይነት ጭቈናና እስራት፣ እንዲሁም ከኀጢአት ባርነት ያለ ጥርጥር ነጻ እንደሚያወጣ ያመ ለክታል::

1፥76 *የልዑል ነቢይ ትባላለህ፤* ኢየሱስ ግን፣ "የልዑል ልጅ" ይባላል (ቍ 32 እና ማብ ይመ):: *መንገድ ለማዘጋጀት፤* የ3፥4 ማብ ይመ::

1፥78 *የንጋት ፀሓይ፤* የመሲሑን መምጣት ያመለክታል (በዘኍ 24፥17፤ ኢሳ 9፥2፤ 60፥1፤ ሚል 4፥2 ላይ የተገለጹትን ሥዕላዊ አገላለጽ ይመ):: ዘካርያስ ያመሰገነው፣ "የልዑል ነቢይ" የተባለውን ልጁን ብቻ አይደለም (ቍ76-77)፤ የሚመጣውን መሢሕንም አክብሮታል (ቍ 78-79)::

1፥79 *በጨለማ ለሚኖሩት፤* ከእግዚአብሔር ተለይተው የጠፉትን ማለት ነው (ኢሳ 9፥1-2፤ ማቴ 4፥16):: ሰላም፤ የ2፥14 ማብ ይመ::

1፥80 *በይፋ እስከ ታየበት፤* ዮሐንስን በይፋ እንዲታወቅ ያደረገው፣ ስብከቱና የመሢሑን መምጣት ማወጁ ነው፤ አገልግ ሎቱን በጀመረበት ጊዜም ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ሳይሆን አይቀርም (የ3፥23 ማብ ይመ):: *በበረሓ ኖረ፤* ወላጆቹ በሽምግልናቸው የወለዱት ከመሆኑም የተነሳ በልጅነቱ ስለሞቱ ያደ ገው በኢየሩሳሌምና በሙት ባሕር መካከል ባለው ምድረ በዳ ሳይሆን አይቀርም::

2፥1 ዘመንን በተመለከተ ከዓለም ታሪክ ጋር በማዛመድ ትረካውን ያቀረበ የወንጌል ጸሐፊ፣ ሉቃስ ብቻ ነው:: *እንዲቈጠር፤* ለውትድርና አገልግሎትና ቀረጥ ለማስከፈል የተደረገ ቈጠራ ነው፤ ሆኖም አይሁድ ከሮም የውትድርና አገልግሎት ነጻ ነበሩ:: እግዚአብሔር እንዲቈጠር የአረማዊውን ንጉሥ ዐዋጅ በመጠቀም፣ በሚክ 5፥2 ላይ የተገለጸው ትንቢት እንዲፈጸም አደረገ:: *አውግስጦስ ቄሳር፤* በብዙዎች ዘንድ እንደሚታመነው፣ የመጀመሪያውና ታላቅ የሆነው የሮም ንጉሥ ነበር (ከ31 ዓ.ቅ.ክ- 14 ዓ.ም):: የሪፐብሊክ የአገዛዝ ሥርዐትን፣ በንጉሠ ነገሥት የአገዛዝ ሥርዐት በመተካት፣ ግዛቱን በመላው ሜድትራኒያን አካባቢ በማስፋፋት፣ በእርሱ የአገዛዝ ዘመን ዝነኛ የሆነውን "የሮም የሰላም ዘመን" የመ ሰረተው እርሱ ነው:: ለሮም የሥነ ጽሑፍና የሕንፃ ሥራ ወርቃማ ዘመን መጀመር ምክንያትም ነበር:: አውግስጦስ ማለት "ከፍ ያለ" ማለት ሲሆን፣ ይህ የማዕረግ ስም የተሰጠው በ27 ዓ.ቅ.ክ. በሮም መወሰኛ ምክር ቤት በተደረገ የድምፅ ብልጫ ነው::

2፥2 *ቄሬኔዎስ፤* ምናልባት ይህ ባለ ሥልጣን፣ በኀላፊነት ቦታ ላይ ተቀምጦ የነበረው፣ ለሁለት የአገልግሎት ዘመን ሳይ ሆን አይቀርም፤ የመጀመሪያው ከ6-4 ዓ.ቅ.ክ ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ ከ6-9 ዓ.ም ነው:: እያንዳንዱ የሥልጣን ዘመኑም፣ ከሕ ዝብ ቈጠራ ጋር የተያያዘ ነው:: በዚህ ቍጥር ላይ የተጠቀሰው የመጀመሪያው የሕዝብ ቈጠራ ሲሆን፣ በሐሥ 5፥37 ላይ የተጠ ቀሰው ግን፣ ሁለተኛ ቈጠራ ነው::

2፥3 *ወደየራሱ ከተማ፤* ምናልባት ወደ አባቶቻቸው የት ውልድ ከተማ ሊሆን ይችላል::

2፥4 *ናዝሬት ... ቤተ ልሔም፤* ዳዊት ከተወለደበት የቤተ ልሔም ከተማ (1ሳሙ 17፥12፤20፥6)፣ እስከ፣ ናዝሬት፣ ቢያንስ በእግር ሦስት ቀን ያህል ያስኬዳል:: *ይሁዳ፤* በግሪክና በሮ ማውያን ዘመነ መንግሥት፣ የፓሌስቴናን ደቡባዊ ክፍል ማለት ነው፤ ቀደም ሲል ግን በይሁዳ መንግሥት ታቅፎ ነበር::

2፥5 *እጮኛው፤* የማቴ 1፥18 ማብ ይመ:: *ከማርያም ጋር፤* ምናልባት ከዳዊት ዘር በመሆኗ፣ ምዝገባው ሳይመለከታት አይ ቀርም:: የሮም ግዛት የሆነችው ፓሌስቲና በምትገኝባት በሶሪያ ዕድሜ አቸው ዐሥራ ሁለትና ከዚያም በላይ የሆናቸው ሴቶች፣ ግብር እንዲከፍሉና እንዲመዘገቡ ይጠየቁ ነበር::

2፥7 *በጨርቅም፤* አዲስ የተወለደ ሕፃንን በጨርቅ መጠቅለል የተለመደ ነበር:: *በግርግም፤* እንስሳቱ በሚያድሩበት ቦታ ማለት ነው፣ ክርስቶስ በበረት መወለዱን የሚያመለክተው ይህ ብቻ ነው:: ይህ እንደ በረት ያገለግል የነበረ ዋሻ እንደ ሆነ በአፈ ታሪክ ይነገራል::

2፥8 *በሜዳ የሚያድሩ፤* ደረቅ የሆነ የፀደይ ወር ነው ማለት አይደለም፤ ለቤተ መቅደስ መሥዋዕት የመጡ መንጎች፣ቤተ ልሔም አጠገብ በሚገኘው ሜዳ ላይ ዓመቱን ሙሉ ይሰማሩ ነበር፤ ስለዚህ እረኞቹም በዚያ ይውሉና ያድሩ ነበር:: *ሲጠብቁ፤* ከሌባና ከነ ጣቂ አውሬ ማለት ነው::

2፥9 *የጌታም መልአክ፤* በ1፥11፤ በማቴ 1፥20፡ 24፤ 2፥13-19 በተገለጡት የልደት ትረካዎች ውስጥ መልአኩ የተጠራው በዚህ ስም ሲሆን፣ በ1፥11 ላይ ግን ይህ መልአክ ገብርኤል እንደ ሆነ ተጠቅሶአል (1፥19፤ 1፥26 ይመ)::

2፥10 *አትፍሩ፤* መልአክ ሲመለከቱ መፍራት የተለመደ በመሆኑ (የ1፥13 ማብ ይመ)፣ የሚያበረታታ ቃል አስፈላጊ ነበር::

2፥11 *በዳዊት ከተማ፤* በቤተ ልሔም ማለት ነው:: *መድ ኅን፤* አብዛኞቹ አይሁዳውያን ከሮም አገዛዝ ነጻ የሚያወጣቸውን መድኅን፤ የፖለቲካ መሪ ይፈልጉ የነበረ ሲሆን፣ የቀሩት ደግሞ ከበሽታና ከኑሮ ውጣ ውረድ ነፃ የሚያወጣቸውን መድኅን ይፈ ልጉ ነበር፤ በዚህ ቦታ የተጠቀሰው መድኅን ግን ከኀጢአትና ከሞት ነፃ የሚያወጣ ነው (ማቴ 1፥21፤ ዮሐ 4፥42 ይመ):: ጌታ

ክርስቶስ[a] ነው:: [12]ይህ ምልክት ይሁናችሁ፤ ሕፃን ልጅ በጨርቅ ተጠቅልሎ በግርግም ተኝቶ ታገኛላችሁ::"

[13]ድንገትም ብዙ የሰማይ ሰራዊት ከመል አኩ ጋር ታዩ፤ እግዚአብሔርንም እያመሰገኑ፣ እንዲህ አሉ፤

[14]"ክብር በአርያም ለእግዚአብሔር፣ ሰላምም እርሱ ለሚወዳቸው ሰዎች በምድር ይሁን!"

[15]መላእክቱ ከእነርሱ ተለይተው ወደ ሰማይ ከወጡ በኋላ እረኞቹ፣ "ጌታ የገለጠልንን ይህን የሆነውን ነገር እንድናይ ወደ ቤተ ልሔም እንሂድ" ተባባሉ::

[16]እነርሱም ፈጥነው ሄዱ፤ ማርያምንና ዮሴፍን፣ ሕፃኑንም በግርግም ተኝቶ አገኙ:: [17]ካዩም በኋላ፣ ስለ ሕፃኑ የተነገራቸውን ገልጠው አወሩ:: [18]ይህንንም የሰሙ ሁሉ እረኞቹ በነገሯቸው ነገር ተደነቁ፤ [19]ማርያም ግን ይህንን ሁሉ በልቧ ይዛ ታሰላስል ነበር:: [20]እረኞቹም ሁሉም ነገር እንደ ተነገራቸው ሆኖ በማግኘታቸው፣ ስለ ሰሙትና ስላዩት ሁሉ እግዚአብሔርን እያከበሩና እያመሰገኑ ተመ ለሱ::

## ሕፃኑን ኢየሱስ ወደ ቤተ መቅደስ ወሰዱት

[21]ስምንት ቀን ሆኖት የመገረዣ ጊዜው ሲደ ርስ፣ ከመፀነሱ በፊት መልአኩ ባወጣለት ስም ኢየሱስ ተባለ::

[22]በሙሴ ሕግ መሠረት፣ የመንጻታቸው ወቅት በተፈፀመ ጊዜ፣ ዮሴፍና ማርያም ሕፃኑን ለጌታ ለማቅረብ ወደ ኢየሩሳሌም ይዘውት ወጡ፤ [23]ይኸውም በጌታ ሕግ፣ "ተባዕት የሆነ በኵር ሁሉ ለጌታ የተቀደሰ ይሆናል" ተብሎ እንደ ተጻፈ ለመፈጸምና [24]ደግሞም በጌታ ሕግ፣ "ሁለት ዋኖሶች ወይም ሁለት የርግብ ጫጩቶች እንደ ተባለ፣" መሥዋዕት ለማቅረብ ነበር::

[25]በዚያን ጊዜ ጻድቅና ትጉሕ የሆነ ስም ዖን የሚባል አንድ ሰው በኢየሩሳሌም ይኖር ነበር፤ እርሱም የእስራኤልን መጽናናት የሚጠባበቅና መንፈስ ቅዱስ በላዩ ያደረ ሰው ነበር:: [26]ደግሞም የጌታን መሲሕ ሳያይ እንደማይሞት በመንፈስ ቅዱስ ተገ ልጦለት ነበር፤ [27]እርሱም በዚህ ጊዜ በመ ንፈስ ተመርቶ ወደ ቤተ መቅደስ ገባ፤ የል ጁም ወላጆች በሕጉ ልማድ መሠረት ተገቢውን ሊፈጽሙለት ሕፃኑን ኢየሱስን ይዘው በገቡ ጊዜ፣ [28]ስምዖን ተቀብሎ ዐቀፈው፤ እግዚአብሔርን እያመሰገነ እንዲህ አለ፤

[29]"ጌታ ሆይ፤ ቃል በገባኸው መሠረት፣<br>
 አሁን ባሪያህን በሰላም አሰናብተው፤<br>
[30]ዐይኖቼ በሰዎች ሁሉ ፊት ያዘጋጀኸውን፣<br>
 [31]ማዳንህን አይተዋልና::<br>
[32]ይህም ለአሕዛብ መገለጥን የሚሰጥ ብርሃን፣<br>
 ለሕዝብህ ለእስራኤልም ክብር ነው::"

[33]አባቱና እናቱም ስለ እርሱ በተነገረው ነገር ተገረሙ:: [34]ስምዖንም ባረካቸው፤ እና ቱን ማርያምንም እንዲህ አላት፤ "ይህ ሕፃን በእስራኤል ለብዙዎች መነሣትና መውደቅ ምክንያት እንዲሆን፣ ደግሞም ክፉ ለሚያ ስወሩበት ምልክት እንዲሆን ተወስኖአል፤ [35]የብዙዎችም የልብ ሐሳብ የተገለጠ እንዲሆን፣

[a]11 ወይም መሲሕ፤ *ክርስቶስ* (በግሪክ) *መሲሕ* (በዕብራይስጥ) ማለት ሲሆን የሁለቱም ትርጒም *የተቀባ* ማለት ነው፤ እንዲ ሁም ቍ 26 ይመ

2፥12 1ሳሙ 2፥34፤ 10፥7፤1ነገ19፥29፤ መዝ86፥17፤ኢሳ 7፥14
2፥14 ኢሳ9፥6፤ 52፥7፤53፥5፤ሚክ5፥5 ፤ሉቃ1፥79፤ዮሐ14፥27፤ሮሜ5፥1፤ ኤፌ2፥14:17
2፥16 ቍ 7
2፥19 ቍ 51
2፥20 ማቴ9፥8
2፥21 ሉቃ1፥31፤ 59
2፥22 ዘሌ12፥2-8
2፥23 ዘፀ13፥2: 12:15፤ዘኍ3፥13
2፥24 ዘሌ12፥8
2፥25 ቍ38፤ኢሳ 52፥9፤ሉቃ1፥6፤23፥5
2፥27 ቍ22
2፥29 ቍ26፤ሐሥ 2፥24
2፥30 ኢሳ40፥5፤ 52፥10፤ሉቃ3፥6
2፥32 ኢሳ42፥6፤ 49፥6፤ሐሥ13፥47፤ 26፥23
2፥34 ኢሳ8፥14፤ ማቴ12፥46፤21፥44፤ 1ቆሮ1፥23፤ 2ቆሮ2፥16፤ገላ5፥11፤ 1ጴጥ2፥7:8

በዚህ የማዕረግ ስም አስቀድሞ ይጠራ የነበረው እግዚአብሔር ነው፤ በኋላ ግን መሲሑም በዚሁ የማዕረግ ስም ተጠርቷል (ሐሥ 2፥36፤ ፊል 2፥11 ይመ):: *ክርስቶስ፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ::

*2፥14፤* የ1፥46-55 ማብ ይመ:: *መላእክት* ለእግዚአብሔር ምስጋና በማቅረብ፣ የእርሱን ክብርና ግርማ መስከሩ *በአርያም፤* የእግዚአብሔር ማደሪያ የሆነውን ሰማይ ያመለክታል (ከማቴ 6፥9 ጋር ያነጻጽሩ):: *ሰላምም እርሱ ለሚወዳቸው ሰዎች በም ድር ይሁን፤* ሰላም እንደሚሰጣቸው ተስፋ የተገባላቸው ለሁሉ ሳይሆን፣ እግዚአብሔር ደስ ለሚሰኝባቸው ብቻ ነው፤ ሰላም የተ ሰጣቸውም እግዚአብሔር ደስ ለተሰኘባቸው ብቻ ነው (ሉቃስ "ደስ ይለኛል" 3፥22 "በጎ ፈቃድ" በ10፥21 "መልካም ፈቃድ" 12፥32 ሐረጎች እንዴት እንደተጠቀመባቸው ይመ):: የሮም ግዛት፣ በሮም የሰላም ዘመን የነበረው ሰላም፣ ውጫዊ ብቻ ነበር:: መላእክት ግን፣ ከዚህ ይልቅ ጥልቅና ዘላቂ የሆነውን ሰላም ዐወጁ፤ ይህም በመሢሑ በኩል እውን የሆነው የአእምሮና የነፍስ ሰላም ነው (ቍ 11):: ከእግዚአብሔር ጋር ሰላም የሚገኘው፣ በክርስቶስ በማ መን ነው (ሮሜ 5፥1)፤ "እርሱ ለሚወዳቸው" የተባለላቸው፣ አማ ኞች ናቸው:: ከዳዊት ዘር የሆነው መሢሕ፣ "የሰላም አለቃ" ተብሎአል (ኢሳ 9፥6)፤ ክርስቶስም ለደቀ መዛሙርቱ ሰላም እንደሚሰጣቸው ቃል ገብቶላቸዋል (ዮሐ 14፥27):: በሌላ በኩል ደግሞ፣ ራሱ ክርስቶስ መለያየትን አምጥቷል ("ሰይፍ" የሚለውን ቃል ማቴ 10፥34-36 ይመ፤ ከሉቃ 12፥49 ጋር ያነጻጽሩ):: ከእ ግዚአብሔር ጋር ሰላም ማግኘት፣ ከሰይጣንና ከሥራው ጋር ተቃ ውሞን ያስከትላልና (ያዕ 4፥4)::

2፥20 *እግዚአብሔርን... እያመሰገኑ፤* ሉቃስ ብዙ ጊዜ የተጠቀመበት አባባል ነው (1፥64፤ 2፥13:28፤ 5፥25-26፤ 7፥16፤ 13፥13፤ 17፥15፤ 18፤ 18፥43፤ 19፥37፤ 23፥47፤ 24፥53)::

2፥22 *የመንጻታቸው፤* አንዲት ሴት ወንድ ልጅ ከወለደች በኋላ፣ የመንጻት ሥርዐት ለመፈፀም ወደ ቤተ መቅደስ ሄዳ መሥዋዕት ከማቅረቧ በፊት፣ አርባ ቀን መቆየት ነበረባት:: የበግ ጠቦትና ርግብ (ዋኖስ) ለማቅረብ ባትችል፣ ሁለት ርግቦች (ዋኖሶች) ማቅረብ ይኖርባታል (ዘሌ 12፥2-8፤ ከዘሌ 5፥11 ጋር ያነጻጽሩ) *ለጌታ ለማቅረብ (ሕፃኑን)፤* የሰውም ሆነ የእንስሳ በኵር "ለጌታ የተቀደሰ" *ነው* (ቍ 23፤ ዘፀ 13፥12-13 ይመ):: በዚህ መልክ ይቀርቡ የነበሩት የእንስሳ በኵር መሥዋዕት ሲሆን፣ በኵር የሆኑ ሰዎች ግን፣ ዕድሜ ልካቸውን እግዚአብሔርን ያገ ለግላሉ:: በመላው እስራኤል በኵር በሆኑ ወንዶች ፈንታ ግን፣ ሌዋውያን ምትክ ሆነው ያገለግሉ ነበር (ዘኍ 3፥11-13፤ 8፥17-18 ይመ) :: *ወደ ኢየሩሳሌም፤* በቤተ ልሔምና በኢየሩሳሌም መካ ከል ያለው ርቀት 8 ኪ.ሜ. ነው::

2፥25 *የእስራኤልን መጽናናት፤* መሢሑ በመጣ ጊዜ፣ ለሕዝቡ የሚያመጣውን መጽናናት ያመለክታል (ቍ 26:38፤ 23፥51፤ 24፥21፤ ኢሳ 40፥1-2፤ ማቴ 5፥4 ይመ):: *መንፈስ ቅዱ ስም ያደረበት፤* በእርሱ ላይ መንፈስ ቅዱስ ያደረው፣ ከጰንጠ ቆስጤ ቀን በኋላ በአማኞች ሁሉ ላይ ባደረበት ሁኔታ አልነበ ረም፤ ሆኖም ስምዖን፣ "ክርስቶስን" ያውቅ ዘንድ መንፈስ ቅዱስ ዕው ቀት ሰጥቶታል::

*2፥29-32፤* የ1፥46-55 ማብ ይመ::

2፥30 *በሰዎች ሁሉ፤* ራሱ ሉቃስ ከአሕዛብ ወገን በመሆኑ፣ ድነት የተሰጠው ለአሕዛብ (ቍ 32) እንዲሁም ለአይሁድ መሆ ኑን በጥንቃቄ በአጽንዖት አመልክቶአል::

2፥33 *አባቱ፣* ሉቃስ፣ ዮሴፍን አባት ማለቱ ኢየሱስ ከድ ንግል መወለዱን ዘንግቶ አይደለም (1፥26-35)::

2፥34 *በእስራኤል ለብዙዎች መነሣትና መውደቅ፤* በእርሱ የሚያምኑትን ክርስቶስ ያነሣቸዋል፤ ለማያምኑበት ግን የማሰ ናከያ ዐለት ነው (20፥17-18፤ 1ቆሮ 1፥23፤1ጴጥ 2፥6-8 ይመ):: *ለብዙዎች... ምክንያት እንዲሆን፤* ክርስቶስ ወደ አባቱ ያመለክ ታል፤ እንዲሁም አብ ለኀጢአተኞች ያለውን ፍቅር ያሳያል፤ ስለ ዚህ እርሱን የሚቃወሙ አብን ይቃወማሉ ማለት ነው::

የአንቺም ነፍስ ደግሞ በሰይፍ ይወጋል።”

[36]ደግሞም ከአሴር ወገን የሆነች የፋኑ ኤል ልጅ፣ ሐና የምትባል ነቢይት በዚያ ነበረች፤ እርሷም በባም አርጅታ ነበር፤ በድ ንግልናዋ ካገባችው ባሏም ጋር ሰባት ዓመት የኖረች ነበረች፤ [37]ዕድሜዋም ሰማንያ አራት ዓመት[ m] እስኪሆናት ድረስ ቀንና ሌሊት ከቤተ መቅደስ ሳትለይ፣ በጾምና በጸሎት የምታገለግል መበለት ሆና ቈየች። [38]በዚያ ኑም ጊዜ ቀርባ እግዚአብሔርን አመሰገነች፤ የኢየሩሳሌምንም መቤዠት ለሚጠባበቁ ሁሉ ስለ ሕፃኑ ተናገረች።

[39]ዮሴፍና ማርያም በጌታ ሕግ የታዘ ዘውን ሁሉ ከፈጸሙ በኋላ፣ በገሊላ አውራጃ ወዳለችው ከተማቸው ወደ ናዝሬት ተመ ለሱ። [40]ሕፃኑም እያደገና እየጠነከረ ሄደ፤ በጥበብ ተሞላ፤ የእግዚአብሔርም ጸጋ በእርሱ ላይ ነበረ።

## ኢየሱስ በዐሥራ ሁለት ዓመቱ ወደ ቤተ መቅደስ ሄደ

[41]ወላጆቹም በየዓመቱ ለፋሲካ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ይሄዱ ነበር። [42]ልጁም ዐሥራ ሁለት ዓመት በሆነው ጊዜ፣ እንደ ተለመ ደው ወደ በዓሉ ወጡ። [43]በዓሉን ከፈጸሙ በኋላ፣ ወደ ቤታቸው ሲመለሱ፣ ብላቴናው ኢየሱስ በኢየሩሳሌም ቀረ፤ ወላጆቹ ግን መቅረቱን አላወቁም ነበር። [44]አብሮአቸው ያለ መስሎአቸው፣ የአንድ ቀን መንገድ ተጓዙ፤ በኋላ ግን ከዘመዶቻቸውና ከወዳጆ ቻቸው ዘንድ ይፈልጉት ጀመር፤ [45]ባጡትም ጊዜ እየፈለጉት ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሱ።

[46]ከሦስት ቀንም በኋላ፣ በመምህራን መካ ከል ተቀምጦ ሲያዳምጣቸውና ጥያቄ ሲያ ቀርብላቸው በቤተ መቅደስ ውስጥ አገ ኙት፤ [47]የሰሙትም ሁሉ በማስተዋሉና በመ ልሱ ይደነቁ ነበር። [48]ወላጆቹም ባዩት ጊዜ ተገረሙ፤ እናቱም፣ “ልጄ ሆይ፤ ለምን እን ዲህ አደረግኸን? አባትህና እኔኮ ተጨን ቀን ስንፈልግህ ነበር” አለችው።

[49]እርሱም፣ “ለምን ፈለጋችሁኝ? በአባቴ ቤት መገኘት እንደሚገባኝ አላወቃችሁ ምን?” አላቸው። [50]እነርሱ ግን የተናገራቸው ነገር አልገባቸውም።

[51]ከዚያም አብሮአቸው ወደ ናዝሬት ወረደ፤ ይታዘዝላቸውም ነበር። እናቱም ይህን ሁሉ ነገር በልቧ ትጠብቀው ነበር። [52]ኢየሱስም በጥበብና በቁመት በሞገስም በእግዚአብሔርና በሰው ፊት አደገ።

## የመጥምቁ ዮሐንስ ስብከት

3፥2-10 ተጓ ምብ - ማቴ 3፥1-10፤ ማር 1፥3-5
3፥16-17 ተጓ ምብ - ማቴ 3፥11:12፤ ማር 1፥7:8

**3** ጢባርዮስ ቄሣር በነገሠ በዐሥራ አምስ ተኛው ዓመት፣ ይኸውም ጳንጥዮስ ጲላ ጦስ የይሁዳ ገዥ፣ ሄሮድስ የገሊላ አራት ኛው ክፍል ገዥ፣ ወንድሙ ፊልጶስ የኢጡር ያስና የጥራኮኒዶስ የአራተኛው ክፍል ገዥ ሊሳኒዮስም የሳቢላኒስ አራተኛው ክፍል ገዥ

2፥36 ሐሥ21፥9
2፥37 ሐሥ13፥3፤ 14፥23፤1ጢሞ5፥5:9
2፥38 ቍ 25፤ ኢሳ 40፥2፤52፥9፤ ሉቃ1፥68፤24፥21
2፥39 ቍ51፤ ማቴ2፥23
2፥40 ቍ52፤ ሉቃ1፥80
2፥41 ዘፀ23፥15፤ ዘዳ16፥1-8፤ ሉቃ22፥8
2፥47 ማቴ7፥28
2፥48 ማቴ12፥46፤ ሉቃ3፥23፤4፥22
2፥49 ዮሐ2፥16
2፥50 ማር9፥32
2፥51 ቍ19:39፤ ማቴ 2፥23
2፥52 ቍ40፤ 1ሳሙ2፥26፤ ምሳ3፥4፤ሉቃ1፥80
3፥1 ማቴ14፥1፤ 27፥2

[m]37 ወይም *ለሰማንያ አራት ዓመት መበለት የነበረች*

2፥35 *የአንቺም ነፍስ ደግሞ በሰይፍ ይወጋል፤* “የአን ቺም” የሚለው ቃል፣ ማርያም ጥልቅ ሥቃይ እንደምትቀበል የሚያመለክት ነው፤ በሉቃስ ወንጌል ለመጀመሪያ ጊዜ የክርስቶስ ሥቃይና ሞት ተጠቅሶ የሚገኘው በዚህ ቍጥር ነው።

2፥36 *ነቢይት፤* በነቢይነት የሚታወቁ ሌሎቹ ሴቶች ማርያም (ዘፀ 15፥20)፣ ዲቦራ (መሳ 4፥4 ሕልዳናና) (2ነገ 22፥14) የፊልጶስ ሴቶች ልጆች (ሐሥ 21፥9) ናቸው። *ሐና፤* ይህ በብሉይ ኪዳን ከተጠቀሰው ስም ጋር (1ሳሙ 1፥2) ተመሳሳይ ሲሆን፣ ትርጕሙም “ጸጋን የተሞላ” ማለት ነው። ሐና ስለ ሕፃኑ ሳሙኤል እግዚአብሔርን እንደ አመሰገነች ሁሉ (1ሳሙ 2፥1-10)፣ ይህችኛዋ ሐናም ስለ ሕፃኑ ኢየሱስ እግዚአብሔርን አመሰገነች።

2፥37 *ከቤተ መቅደስ ሳትለይ፤* ሄሮድስ ያሠራው ቤተ መቅደሱ እጅግ ትልቅ በመሆኑ፣ በውስጡ ለልዩ ልዩ አገልግሎት የሚውል ክፍሎች ነበሩት፤ ሐናም ከእነዚሁ ክፍሎች በአንዱ እንድትኖር ተፈቅዶላት ይሆናል። ምናልባት ይህ ሐረግ የሚያ መለክተው፣ ዘወትር በቤተ መቅደስ ሐና እግዚአብሔርን እንደ ምታመልክ ይሆናል።

2፥38 *ኢየሩሳሌም፤* የተመረጡ የእግዚአብሔር ሰዎች ቅድ ስት ከተማ ናት (ኢሳ 40፥2፤ 52፥9)፤ እዚህ ላይ ግን መላው እስ ራኤልን ለማመልከት ነው።

2፥39 *ገሊላ... ተመለሱ፤* ሉቃስ፣ የሰብአ ሰገልን መም ጣት፣ ሄሮድስ ሕፃኑ ኢየሱስን ለመግደል ያደረገውን ሙከራ፣ እንዲሁም ወደ ግብጽ አገር የተደረገውን ሽሽትና ከዚያም መመ ለሳቸውን አልጻፈም (ከማቴ 2፥1-23 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥41 *ፋሲካ በዓል፤* በየዓመቱ የሚከበሩትን ሦስት በዓላት ወንዶች ሁሉ (የቤተ ሰብ ኀላፊ የሆነው ቤተ ሰቡን ጨምሮ) ተገኝተው እንዲያከብሩ ሕጉ ያዝ ነበር፤ እነዚህ በዓላትም ፋሲካ፣ ጴንጤቆስጤና የዳስ በዓል ናቸው (የዘፀ 23፥14-17፤ የዘዳ 16፥16 ማብ ይመ)። የቦታ ርቀት ሦስቱን በዓላት በኢየሩሳሌም ተገኝቶ ለማክበር ባያስችልም፣ ብዙ አይሁዳውያን ግን በተቻላቸው መጠን በፋሲካ በዓል ላይ ይገኙ ነበር።

2፥46 *ሦስት ቀን፤* የመጀመሪያው ቀን ከኢየሩሳሌም ወደ ቤታቸው የተጓዙበት፣ ሁለተኛው እንደ ገና ወደ ኢየሩሳሌም የተ መለሱበት ሲሆን፣ ሦስተኛው ደግሞ እርሱን ሲፈልጉ የቈዩበት ነው። *መምህራን፤* የአይሁድ ሃይማኖትና ባህል ሊቃውንት ናቸው።

2፥49 *በአባቴ ቤት፤* በሰማይ የሚኖረው አባቱ የሰጠውን አደራ ኢየሱስ፤ አመለከተ፥ እርሱ “አባቴ” ያለው፣ ማርያም “አባ ትህ” ካለችው የተለየ መሆኑን ገለጸ (ቍ 48)። ገና በዐሥራ ሁለት ዓመቱ ከአብ ጋር ያለው ልዩ ግንኙነት ምን እንደ ሆነ ያውቅ ነበር። ያም ሆኖ ለምድራዊ ወላጆቹ ታዛዥ ነበር። (ቍ 51)።

*2፥52፤* ሉቃስ፣ የ1ሳሙ 2፥26 አገላለጽን በመውሰድ እዚህ ላይ የጻፈ ይመስላል። *ኢየሱስም ...አደገ፤* ምንም እንኳ ኢየሱስ አምላክ ቢሆንም፣ ሰው ሆኖ ከተወለደበት ጊዜ ጀምሮ እውቀት ሁሉን ጥበብ እንደነበረው የሚያመላክት ምንም ማስረጃ ማቅረብ አይቻልም፤ ስለዚህም በሰው ላይ የሚታየው የዕድገት ደረጃ በእርሱ ላይም ታይቷል።

*3፥1-2፤* አብዛኛውን ጊዜ ታሪክ ጸሐፊዎች አንድ ሁኔታ የተከናወነበትን የሚያመለክቱት፣ ሁኔታው በተከናወነበት ወቅት የነበረውን የሀገር መሪ ዘመነ መንግሥት በመጥቀስ ነው።

3፥1 *በዐሥራ አምስተኛው ዓመት፤* በዚህ ገለጻ መሠረት የተለያዩ አማራጭ ዘመኖች ሊጠቀሱ ይቻላሉ፤ ሆኖም ከ25-26 ዓ.ም ያለው ጊዜ ብቻ ከኢየሱስ የምድር ላይ ሕይወት ጋር ይስማማል። (ጢባርዮስ በግዛቶቹ ላይ ሥልጣን የነበረው ከ11 ዓ.ም ጀምሮ ነበር)። በዚህ ቍጥር ላይ የተጠቀሱት ሌሎቹ መሪዎች ስለዚህ ታሪካዊ ጊዜ አጠቃላይ ግንዛቤ ይሰጣል እንጂ፣ የመ ጥምቁ ዮሐንስ አገልግሎት መቼ እንደ ተጀመረ ለማወቅ አይጠ ረዳንም። *ጳንጥዮስ ጲላጦስ፤* ይሁዳን፣ ሰማርያንና ኤዶምያስን የገዛ ሮማዊ ገዥ ነው። *ሄሮድስ የገሊላ አራተኛው ክፍል ገዥ፤* ታላቁ ሄሮድስ ከሞተ በኋላ፣ ልጆቹ አርኬላዎስ፣ ሄሮድስ አን ቲጳስና ሄሮድስ ፊሊጶስ። በተከፈለው ግዛቱ ላይ ገዥዎች ሆኑ። ስለዚህም ሄሮድስ አንቲጳስ የገሊላና የፔሪያ አገረ ገዥ ሆነ (የ ማቴ 14፥1 ማብ ይመ)። *ሊሳኒዮስም የሳቢላኒስ አራተኛው ክፍል ገዥ፤* በጥቂት ጽሑፎች ላይ ስሙ ተጽፎ ከመገኘቱ በቀር፣ ስለ እርሱ የሚታወቅ ነገር የለም።

በነበሩበት ጊዜ፣ [2]ሐናና ቀያፋም ሊቃነ ካህናት ሳሉ፣ የእግዚአብሔር ቃል ወደ ዘካርያስ ልጅ ወደ ዮሐንስ በምድረ በዳ መጣ:: [3]እርሱም ለኀጢአት ስርየት የሚሆን የንስሓን ጥምቀት እየሰበከ በዮርዳኖስ ወንዝ አካባቢ ወዳሉት ስፍራዎች ሁሉ መጣ፤ [4]ይኸውም ነቢዩ ኢሳይያስ በመጽሐፉ እንዲህ ሲል በጻፈው ቃል መሠረት ነበር፤

"በበርሓ እንዲህ ብሎ የሚጮኽ ሰው ድምፅ፤
 'የጌታን መንገድ አዘጋጁ፤
  ጐዳናውንም አቅኑ፤
[5]ሸለቆው ሁሉ ይሞላል፤
 ተራራውና ኰረብታው ሁሉ ዝቅ ይላል፤
ጠማማው መንገድ ቀና፣
 ሸካራውም ጐዳና ትክክል ይሆናል፤
[6]የሰውም ዘር ሁሉ የእግዚአብሔርን
  ማዳን ያያል::' "

[7]ዮሐንስም በእርሱ እጅ ሊጠመቁ የወጡትን ሰዎች እንዲህ ይላቸው ነበር፤ "እናንት የእፉኝት ልጆች፣ ከሚመጣው ቍጣ እንድትሸሹ ማን መከራችሁ? [8]እንግዲህ ለንስሓ የሚገባ ፍሬ አፍሩ፤ ደግሞም በልባችሁ፣ 'አብርሃም አባታችን አለን' ማለትን አትጀምሩ፤ እግዚአብሔር ከእነዚህ ድንጋዮች ለአብርሃም ልጆች ማስነሣት እንደሚችል እነግራችኋለሁና:: [9]አሁን እንኳ ምሳር በዛፎች ሥር ተቀምጦአል፤ መልካም ፍሬ የማያፈራም ዛፍ ሁሉ ተቈርጦ ወደ እሳት ይጣላል::"

[10]ሕዝቡም፣ "ታዲያ፣ ምን እናድርግ?" ብለው ጠየቁት::

[11]ዮሐንስም፣ "ሁለት ልብስ ያለው ምንም ለሌለው ያካፍል፤ ምግብ ያለውም እንዲሁ ያድርግ" ብሎ መለሰላቸው::

[12]ቀረጥ ሰብሳቢዎችም ሊጠመቁ ወደ እርሱ መጥተው፣ "መምህር ሆይ፤ እኛስ ምን እናድርግ?" አሉት::

[13]እርሱም፣ "ከታዘዛችሁት በላይ ቀረጥ አትሰብስቡ" አላቸው::

[14]ወታደሮች ደግሞ፣ "እኛስ ምን እናድርግ?" ብለው ጠየቁት::

እርሱም፣ "የማንንም ገንዘብ በግፍ አትንጠቁ፤ ሰውንም በሐሰት አትክሰሱ፤ ደመወዛችሁ ይብቃችሁ" አላቸው::

[15]ሕዝቡ በጕጕት እየተጠባበቁ ሳሉ፣ "እርሱ ክርስቶስ ይሆንን?" እያሉ ሁሉም በልባቸው ስለ ዮሐንስ ያሰላስሉ ነበር:: [16]ዮሐንስ ለሁሉም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "እኔ በውሃ አጠምቃችኋለሁ፤ ነገር ግን ከእኔ የሚበረታ ይመጣል፤ እኔም የእርሱን የጫማ ማሰሪያ መፍታት የሚገባኝ አይደለሁም፤ እርሱ በመንፈስ ቅዱስና በእሳት ያጠምቃችኋል፤ [17]ዐውድማውን ፈጽሞ ለማጥራትና ስንዴውንም ወደ ጐተራው ለመክተት መንሹ በእጁ ነው፤ ገለባውን ግን በማይጠፋ እሳት ያቃጥለዋል::" [18]ዮሐንስም በብዙ ሌሎች የምክር ቃላት ሕዝቡን እያስጠነቀቀ ወንጌልን ሰበከላቸው::

[19]ነገር ግን ዮሐንስ፣ የአራተኛውን ክፍል ገዥ ሄሮድስን የወንድሙ ሚስት በነበረችው በሄሮድያዳ ምክንያትና ስለ ሌሎች

3፥2 ማቴ3፥1፤ 26፥3፤ ሉቃ1፥13
3፥3 ቍ16፤ማር1፥4
3፥6 መዝ98፥2፤ኢሳ 40፥3-5፤42፥16፤ 52፥10፤ሉቃ2፥30
3፥7 ማቴ12፥34፤ 23፥33፤ሮሜ1፥18
3፥8 ኢሳ51፥2፤ ሉቃ19፥9፤ዮሐ8፥33፡ 39፤ሐሥ13፥26፤ሮሜ 4፥1:11:12:16:17፤ 9፥7:8፤ገላ3፥7
3፥9 ማቴ3፥10
3፥10 ቍ12:14፤ ሐሥ 2፥37፤16፥30
3፥11 ኢሳ58፥7፤ ሕዝ 18፥7
3፥12 ሉቃ7፥29
3፥13 ሉቃ19፥8
3፥14 ዘፀ23፥1፤ ዘሌ19፥11
3፥15 ማቴ3፥1፤ ዮሐ1፥19:20፤ሐሥ 13፥25
3፥16 ቍ3፤ማር 1፥4፤ዮሐ1፥26:33፤ 11፥16፤19፥4
3፥17 ኢሳ30፥24፤ ማቴ13፥30፤25፥41
3፥19 ቍ1፤ ማቴ14፥1

3፥2 *ሐናና ቀያፋም ሊቃነ ካህናት፤* ከ6 ዓ.ም. ጀምሮ የሮም ባለሥልጣን በሆነው በግራቱስ ከሹመቱ እስከ ተሻረበት እስከ 15 ዓ.ም ድረስ፣ሐና ሊቀ ካህን ነበር:: ከእርሱ በኋላ ልጁ ኤልኤዜር በቦታው ተተካ፤ ቀጥሎም አማቹ ቀያፋና በኋላም ደግሞ የተቀሩት አራቱ ልጆቹ በቦታው ተተኩ:: የሮም ገዥዎች ሐናን ከሥልጣን ቢያወርዱትም፣ አይሁዳውያን ግን እንደ ባለሥልጣን ይቈጥሩት ነበር (ዮሐ 18፥13፤ ሐሥ 4፥6 ይመ)፤ በዚህም ምክንያት፣ ሉቃስ፣ የሐናን ስም በሮም ከተሾመው ቀያፉ ጋር ጨምሮ ጽፎአል:: *የእግዚአብሔር ቃል፤* የዮሐንስ ስብከትና የመጥምቁ ሥልጣን ምንጩ፣ የእግዚአብሔር ቃል ነበር:: ለመጥምቁ ዮሐንስ የእግዚአብሔር መልእክት የመጣው፣ ልክ በብሉይ ኪዳን ለነበሩት ነቢያት በመጣበት ሁኔታ ነበር (ከኤር 1፥2፤ ከሕዝ 1፥3፤ ከሆሴ 1፥1፤ ከኢሳ 1፥1 ጋር ያነጻጽሩ):: *በምድረ በዳ፤* አሸዋማና ውሃ የሌለበትን ቦታ ብቻ ሳይሆን፣ ሰው የማይኖርበትን ባድማ ምድር የሚመለክት ነው::

3፥3 *ለኀጢአት ስርየት፤* በመስቀል ላይ ክርስቶስ ስለሞተ፣ ንስሓ የገባውን ሰው ከኀጢአት ቅጣት ያድነዋል:: *የንስሓን ጥምቀት፤* የማቴ 3፥11 ማብ ይመ:: የዮሐንስ ጥምቀት ትኵረት የሚያደርገው የልብ መለወጥ ሲሆን፣ ከዚህ የተነሣም ስለ ኀጢአት መጸጸትንና በቅድስና ሕይወት ለመመላለስ ቊርጥ ውሳኔ ማድረግንም ያካትታል::

3፥4 *መንገድ አዘጋጁ፤* አንድ ንጉሥ ወደ ሩቅ አገር ጉዞ ከመጀመሩ በፊት፣ የሚጓዝበት መንገድ ይስተካከላል፤ በተመሳሳይ መልኩ በመጥምቁ ዮሐንስ አገልግሎትም በሥነ ምግባርና በመንፈሳዊ ረገድ ለመሲሑ መምጣት ቅድመ ዝግጅት ተደርጐ ነበር፤ ይኸውም፣ ንስሓ በመግባት፣ የኀጢአት ይቅርታና የመድኅን አስፈላጊነትን በማወቅ ላይ ትኵረት ያደረገ ነበር::

3፥6 *ሰውም... ሁሉ፤* የእግዚአብሔርን ማዳን፣ ለአይሁድና ለአሕዛብ እንዲታወቅ መደረግ ነበረበት፤ ይህ ደግሞ የሉቃስ ወንጌል ዐቢይ ሐሳብ ነው (የ2፥31 ማብ ይመ)::

3፥7 *ከሚመጣው ቍጣ፤* በ70 ዓ.ም. የተፈጸመውን የኢየሩሳሌምን መፈራረስና (21፥20-23) የመጨረሻውን ፍርድ ያመለክታል (ዮሐ 3፥36)፤ በተጨማሪም የ1ተሰ 1፥10፤ 5፥9 ማብ ይመ::

3፥9 *ምሳር በ... ሥር፤* በንስሓ መመለሳቸውን የሚያስመሰክር ሕይወት በሌላቸው ሰዎች፣ ላይ በፍጥነት የሚ ደርስባቸው ፍርድ የሚያመለክት፣ ታምራታዊ አባባል ነው:: *እሳት፤* የፍርድ ትእምርት ነው (ማቴ 7፥19፤13፥40-42)::

3፥11 *ሁለት ልብስ፤* እዚህ ላይ (ልብስ) የተባለው፣ እንደ እጀ ጠባብ ዐይነት የሆነውን ነው፤ ሁለት የዚህ ዐይነት እጀ ጠባብ በአንድ ጊዜ ለመልበስ አስፈላጊ ባለመሆኑ፣ ሁለተኛውን ምንም ለሌለው መስጠት አለበት (9፥3 ይመ)::

3፥12 *ቀረጥ ሰብሳቢዎች፤* ግብር ለሮም መንግሥት የሚሰበስበው በአይሁዳውያን ወኪሎች አማካይነት ነበር፤ እነዚህ ወኪሎች፣ አረማዊ የሆነውን መንግሥት በመደገፋቸውና የገዛ ወገኖቻቸውን በማታለላቸው ምክንያት የተጠሉ ነበሩ::

3፥14 *ወታደሮች፤* ለተወሰኑ የአይሁድ ተቋማት፣ መጠነኛ የሆነ ወታደራዊ ኀይል ለጥበቃ ተፈቅዶላቸው ነበር፤ ይኸውም ለሄሮድስ አንቲጳስ፣ ለቤተ መቅደሱና ለቀረጥ ሰብሳቢዎች ነበር:: ዮሐንስ ያወገዘ የነበረው፣ የቀረጥ ሰብሳቢዎቹንና የወታደሮቹን ሙያ ሳይሆን፣ ሥነ ምግባር የጎደለውን ምግባራቸውን ነበር::

3፥16 *በመንፈስ ቅዱስ... ያጠምቃችኋል፤* በጰንጠቆስጤ ቀን ይህ ተፈጽሞአል (ሐሥ 1፥5፤ 2፥4:38):: በእሳት፤ እዚህ ላይ "እሳት" የሚለው ቃል የሚያመለክተው ፍርድን ነው (ቍ 17)፤ እንዲሁም በጰንጠቆስጤ ቀን የታየውን እሳት በሐሥ 2፥3 ላይ፣ የሰውን ሥራ የሚፈትነውን እሳት በ1ቆሮ 3፥13 ላይ ይመ::

3፥17 *መንሹ፤* የሩት 1፥22 ማብ ይመ:: ገለባው የሚያመለክተው ንስሓ ያልገባን ሰው ሲሆን፣ ስንዴው ደግሞ ጻድቅን ሰው ነው:: መሲሑ ሲመጣ የሚፈረድባቸውና የሚቀጡት አሕዛብ ብቻ ናቸው በማለት አብዛኞዎቹ አይሁዳውያን ቢያስቡም፣ ዮሐንስ ግን አይሁዳውያን ቢሆኑም እንኳን ንስሓ በማይገባ በማንኛውም ሰው ላይ ፍርድ እንደሚደርስ በግልጽ ተናገረ::

3፥19 *ሄሮድስን... በሄሮድያዳ ምክንያትና... በገሠጸው፤* ሄሮድስ አንቲጳስ፣ የዐረብ ገዥ የነበረውን የአርጤስ አራተኛን ልጅ ፈትቶ፣ የሌላው የወንድሙ የሄሮድስ ፊልጶስ ሚስት የነበረችውንና የወንድሙ ልጅ የሆነችውን ሄሮዲያዳን ለማግባት ፈለገ (ማቴ 14፥3፤ ማር 6፥17 ይመ)::


ቅድስት አገር በታላቁ
ሄሮድስ ግዛት
37-4 ዓ.ቅ.ክ
የሄሮድስ የተመሸጉ ከተሞች
የሄሮድስ ግዛት ክልል
የማይታወቅ ድንበር
ተራራ
ኢጡርያስ
ባቢላኒስ
ሲዶና
አባና ወንዝ
ደማስቆ
የአርሞንዔም ተራራ
ፋርፋ ወንዝ
ጥሮስ
ፊልጶስ ቂሣርያ
ፊንቄ
ጥራኮኒዶስ
ቢታንያ
ረጳና
አኮ
(ጴጤሌማይስ)
ኮራዚን
ቤተ ሳይዳ
ቅፍርናሆም
የገሊላ ባሕር
ጥብርያዶስ
ድዮን
ያሙክ ወንዝ
ናዝሬት
የታቦር ተራራ
ናይን
ገሊላ
ቀርሜሎስ ተራራ
ዶር
ቂሣርያ
አውራንጢስ
ታላቁ ባሕር
(ሜድትራኒያን)
ቤትሻን
ፔላ
ዐሥር ከተሞች
ሰማርያ
ሰማርያ
የጌባል ተራራ
የገሪዛም ተራራ
ሲካር
ያቦቅ ወንዝ
ዐረቢያ
አንቲጳጥር
ኢዮጴ
አርማትያ
ልዳ
ራማ
ኤፍሬም
ኢያሪኮ
ፊላደልፊያ
ገርዶ
የዮርዳኖስ ወንዝ
ጃምኒያ
ይሁዳ
አሻዶድ
አዛጦን
ኢየሩሳሌም
ቤተልሔም
ቁምራን
የናባው ተራራ
አስቀሎና
መካርዮስ
አርኖን ወንዝ
ሙት ባሕር
ኬብሮን
ጋዛ
ዐረቢያ
ኤዶምያስ
ማሳዳ
ቤርሳቤህ
የናባትያን መንግሥት
ማይልስ
ኪ.ሜ
የሙት ባሕር ጥቅልሎች የተገኙበት
ቁምራን የኤሴኔያውያን ከተማ ነች

ሥራዎቹ በገሠጸው ጊዜ፣ [20]ሄሮድስ ይህን በሌላው ሁሉ ላይ በመጨመር፣ ዮሐንስን ወህኒ ቤት አስገባው።

## የኢየሱስ መጠመቅና የትውልድ ሐረጉ

3፥21፡22 ተጓ ምብ - ማቴ 3፥13-17 ማር 1፥9-11
3፥23-38 ተጓ ምብ - ማቴ 1፥1-17

[21]ሕዝቡ ሁሉ ከተጠመቀ በኋላ ኢየሱስም ተጠመቀ፤ እየጸለየም ሳለ ሰማይ ተከፈተ፤ [22]መንፈስ ቅዱስም በአካላዊ ቅርጽ እንደ ርግብ በእርሱ ላይ ወረደ፤ ከሰማይም፣ "የምወድህ ልጄ አንተ ነህ፤ በአንተ ደስ ይለኛል" የሚል ድምፅ መጣ።

[23]ኢየሱስ አገልግሎቱን ሲጀምር ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ያህል ነበር፤ ሕዝቡም እንደ መሰላቸው የዮሴፍ ልጅ ሆኖ፣
የኤሊ ልጅ፣ [24]የማቲ ልጅ፣
የሌዊ ልጅ፣ የሚልኪ ልጅ፣
የዮና ልጅ፣ የዮሴፍ ልጅ፣
[25]የማታትዩ ልጅ፣ የአሞጽ ልጅ፣
የናሆም ልጅ፣ የኤሲሊም ልጅ፣
የናጌ ልጅ፣ [26]የማአት ልጅ፣
የማታትዩ ልጅ፣ የሴሜይ ልጅ፣
የዮሴፍ ልጅ፣ የዮዳ ልጅ፣
[27]የዮናን ልጅ፣ የሬስ ልጅ፣
የዘሩባቤል ልጅ፣ የሰላትያል ልጅ፣
የኔሪ ልጅ፣ [28]የሚልኪ ልጅ፣
የሐዲ ልጅ፣ የዮሳስ ልጅ፣ የቆሳም ልጅ፣
የኤልሞዳም ልጅ፣ የኤር ልጅ፣
[29]የዮሴዕ ልጅ፣ የኤልዓዘር ልጅ፣
የዮራም ልጅ፣ የማጣት ልጅ፣
የሌዊ ልጅ፣ [30]የስምዖን ልጅ፣
የይሁዳ ልጅ፣ የዮሴፍ ልጅ፣
የዮናም ልጅ፣ የኤልያቄም ልጅ፣
[31]የሜልያ ልጅ፣ የማይናን ልጅ፣
የማጣት ልጅ፣ የናታን ልጅ፣
የዳዊት ልጅ፣ [32]የእሴይ ልጅ፣
የኢዮቤድ ልጅ፣ የቦዔዝ ልጅ፣
የሰልሞን[ሀ] ልጅ፣ የነአሶን ልጅ፣
[33]የአሚናዳብ ልጅ፣ የአራም[ለ] ልጅ፣
የአርኒ ልጅ፣ የኤስሮም ልጅ፣ የፋሬስ ልጅ፣
የይሁዳ ልጅ፣ [34]የያዕቆብ ልጅ፣
የይስሐቅ ልጅ፣ የአብርሃም ልጅ፣
የታራ ልጅ፣ የናኮር ልጅ፣
[35]የሴሮህ ልጅ፣ የራጋው[ሐ] ልጅ፣
የፋሌቅ ልጅ፣ የአቤር ልጅ፣
የሳላ ልጅ፣ [36]የቃይናን ልጅ፣
የአርፋክስድ ልጅ፣ የሴም ልጅ፣
የኖኅ ልጅ፣ የላሜህ ልጅ፣
[37]የማቱሳላ ልጅ፣ የሄኖክ ልጅ፣
የያሬድ ልጅ፣ የመላልኤል ልጅ፣
የቃይናን ልጅ፣ [38]የሄኖስ ልጅ፣
የሤት ልጅ፣ የአዳም ልጅ፣
የእግዚአብሔር ልጅ።

## የኢየሱስ መፈተን

4፥1-13 ተጓ ምብ – ማቴ 4፥1-11፤ ማር 1፥12፡13

**4** ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስ ተሞልቶ ከዮርዳኖስ እንደ ተመለሰ መንፈስ ወደ በረሓ ወሰደው፤ [2]በዚያም አርባ ቀን በዲያብሎስ ተፈተነ፤ በእነዚያም ቀናት ምንም ሳይበላ ቈይቶ በመጨረሻ ተራበ።

3፥20 ማቴ14፥3፡4
3፥21 ማቴ14፥23፤ ማር1፥35፤6፥46፤ ሉቃ5፥16፤6፥12፤9፥18፡28፤11፥1
3፥22 ኢሳ42፥1፤ ማቴ3፥17፤ዮሐ1፥32፡33፤ሐሥ10፥38
3፥23 ማቴ4፥17፤ ሉቃ1፥27፤ሐሥ1፥1
3፥27 ማቴ1፥12
3፥31 2ሳሙ5፥14፤ 1ዜና3፥5
3፥33 ሩት4፥18-22፤1ዜና2፥10-12
3፥34 ዘፍ11፥24፡26
3፥36 ዘፍ5፥28-32፤ 11፥12
3፥37 ዘፍ5፥12-25
3፥38 ዘፍ5፥1፡ 2፡6-9
4፥1 ቍ14፡18፤ሕዝ37፥1፤ሉቃ1፥15፡35፤ 2፥27፤3፥3፡16፡21፡22 ፤10፥21
4፥2 ዘፀ34፥28፤ 1ነገ19፥8፤ዕብ4፥15

[ሀ]32 አንዳንድ የጥንት ቅጆች ሳላ ይላሉ ሌሎች ቅጆች ይለያያሉ
[ለ]33 አንዳንድ ቅጆች የአሚናዳብ ልጅ የአዲም ልጅ የአርኒ ልጅ ይላሉ፤
[ሐ]35 የግሪኩ ቅጅ *'የራጋው'*

3፥20 ***ዮሐንስን ወህኒ ቤት አስገባው፤*** ዮሴፍ ወልደ ኮሪዮን በጻፈው መሠረት፣ ዮሐንስ የታሠረው ከሙት ባሕር በስተ ምሥራቅ ማኬሩስ በተባለው (አንቲኩቲ 18.5.2) ስፍራ ነው። ይኸውም፣ ኢየሱስ አገልግሎት ከጀመረ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ነው (ዮሐ 3፥22-24)፤ ሆኖም እዚህ ላይ ሉቃስ ይህን የጠቀሰው፣ የኢየሱስን አገልግሎት ከመተረኩ በፊት፣ የጀመረውን የዮሐንስን አገልግሎት ትረካ ለመደምደም ስለ ፈለገ ነው (ማቴ 4፥12፤ ማር 1፥14 ይመ)። ይህም ሆኖ ሳለ፣ ስለ ዮሐንስ አሟሟት በሌላ ክፍል በአጭሩ ገልጾአል (9፥7-9)።

3፥21 ***ተጠመቀ፤*** የማቴ 3፥15 ማብ ይመ። ***እየጸለየም ሳለ፤*** በተጠመቀ ጊዜ ኢየሱስ የጸለየ መሆኑን የጻፈው ሉቃስ ብቻ ነው። ሉቃስ በተደጋጋሚ ካቀረባቸው ዐበይት ሐሳቦች አንዱ፣ ኢየሱስ ይጸልይ እንደ ነበር ነው። (5፥16፤ 6፥12፤ 9፥18፡28-29፤ 11፥1፤ 22፥32፡41፤ 23፥34፡46 ይመ)።

3፥22 ***መንፈስ ቅዱስ... ወረደ፤*** በኢየሱስ ላይ መንፈስ ቅዱስ "በአካል መልክ" መውረዱን ሉቃስ ቢጽፍም፣ ይህ ሁኔታ ለዮሐንስ ከእግዚአብሔር ዘንድ የተሰጠ ምልክት ነበር (ዮሐ 1፥32-34፤ እንዲሁም የማር 1፥10 ማብ ይመ)። ***የምወድህ ልጄ አንተ ነህ፤*** መዝ 2፥7፤ ኢሳ 42፥1፤ ዕብ 1፥5 ይመ። ከዚህ ሌላ፣ በሁለት የተለያዩ ጊዜያት ስለ ኢየሱስ ከሰማይ ስለመጣው ድምፅ የወንጌል ጸሓፊዎቹ ገልጸዋል፤ ይኸውም (1) በደብረ ታቦር ተራራ ላይ (9፥35)፣ (2) በኢየሱስ አገልግሎት የመጨረሻ ሳምንት በቤተ መቅደሱ ግቢ ውስጥ ነው (ዮሐ 12፥28)።

***3፥23-38፤*** በሉቃስና በማቴዎስ በቀረበው የዘር ሐረግ ዝርዝር መካከል፣ አንዳንድ ልዩነት አለ (1፥2-16)። ማቴዎስ የዘር ሐረግ ዝርዝሩን የሚጀምረው፣ የአይሁድ ሕዝብ አባት በሆነው ከአብርሃም ነው፤ ሉቃስ ግን ከዮሴፍ ጀምሮ እስከ አዳም ድረስ ያለውን የዘር ሐረግ በመዘርዘር፣ ኢየሱስ ከሰው ዘር ጋር ያለውን ግንኙነት በማመልከት ነው (የ2፥31 ማብ ይመ)። ማቴዎስና ሉቃስ የጻፉት የዘር ሐረግ ዝርዝር፣ ከአብርሃም እስከ ዳዊት ድረስ ተመሳሳይ ነው፤ ከዳዊት በኋላ ባለው የዘር ሐረግ ግን ልዩነት አላቸው። ይህ የሆነበትን ምክንያት አስመልክተው አንዳንድ ምሁራን ማቴዎስ የዘረዘረው ዙፋኑ የወረሱትን የዳዊት ቤት የዘር ሐረግ ተከትሎ ሲሆን፣ ሉቃስ ግን ከዮሴፍ ጀምሮ እስከ ዳዊት ድረስ ያለውን የዘር ሐረግ በመከተል ነው በማለት ይናገራሉ። ሆኖም ተቀባይነት ያለው ሐሳብ ግን፣ ማቴዎስ የጻፈው የዮሴፍን የዘር ሐረግ ተከትሎ ሲሆን፣ ሉቃስ ግን የማርያምን የዘር ሐረግ ተከትሎ ነው። የዘር ሐረግን በእናት በኩል መቍጠር የተለመደ ነገር እንዳልሆነ ሁሉ፣ ከድንግል መወለድም እንዲሁ ከኢየሱስ በቀር ተሰምቶ የማይታወቅ ነው። ሉቃስ፣ "እንደመሰላቸው የዮሴፍ ልጅ" ብሎ መጻፉ (ቍ 23)፣ ኢየሱስ ከድንግል መወለዱን በግልጽ ለማሳየት የተጠቀመበት ስልት ሲሆን (1፥34-35)፣ ይህም የኢየሱስን የዘር ሐረግ ሲዘረዝር፣ በማርያም በኩል መሆኑ ምን ያህል አስፈላጊ እንደ ሆነ ያመለክታል።

3፥23 ***ሠላሳ ዓመት ያህል፤*** ታሪክ ጸሓፊው ሉቃስ፣ የኢየሱስን ይፋ አገልግሎት የጻፈው ከዓለም ታሪክና (ቍ 1-2 ይመ) ከቀረው የኢየሱስ ሕይወት ጋር በማገናዘብ ነው። አንድ ሌዋዊ አገልግሎቱን የሚጀምረው ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ሲሆን ነው (ዘኍ 4፥47)፤ ይህ ዕድሜ ማንኛውም ሰው፣ (ሙሉ ሰው) ነው የሚባልበትም ነው። ***ሕዝቡም... ይመስላቸው ነበር፤*** ቀደም ሲል ሉቃስ፣ ኢየሱስ ከድንግል መወለዱን አረጋግጦአል (1፥34-35)፤ እዚህ ላይ ደግሞ ዮሴፍ የኢየሱስ ወላጅ አባት አለመሆኑን በድጋሚ ግልጽ አድርጎአል።

4፥1 ***በመንፈስ ቅዱስ ተሞልቶ፤*** ሉቃስ፣ ስለ መንፈስ ቅዱስ በአጽንዖት የገለጸው በወንጌሉ ውስጥ ብቻ ሳይሆን (1፥35፡41፡67፤ 2፥25-27፤ 3፥16፡22፤ 4፥14፡18፤ 10፥21፤ 11፥13፤ 12፥10፡12)፣ በሐዋርያት ሥራ ውስጥም ነው። ***ወደ በረሓ፤*** የይሁዳ በረሓ ማለት ነው (ማቴ 3፥1፤ ይመ እንዲሁም የ1፥80 ማብ ይመ)።

4፥2 ***ተፈተነ፤*** የማቴ 4፥1-11፤ ዕብ 2፥18፤ 4፥15 ማብ ይመ። ኢየሱስ፣ አርባ ቀን በጾመ ጊዜ ተፈትኖ እንደ ነበር ሉቃስ ይናገራል፤ በማቴዎስና በሉቃስ የተገለጹት ሦስት ፈተናዎች የቀረቡ

[3]ዲያብሎስም፣ “የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንህ፣ እስቲ ይህ ድንጋይ እንጀራ እንዲሆን እዘዘው” አለው::

[4]ኢየሱስም፣ “ ‘ሰው በእንጀራ ብቻ አይኖርም’ ተብሎ ተጽፎአል” ብሎ መለሰለት::

[5]ከዚያም ዲያብሎስ ወደ አንድ ከፍታ ቦታ አውጥቶት የዓለምን መንግሥታት ሁሉ በቅጽበት አሳየው፤ [6]እንዲህም አለው፤ “የእነዚህ መንግሥታት ሥልጣንና ክብር ሁሉ ለእኔ ተሰጥቶአል፤ እኔም ለምወደው ስለ ምሰጥ፣ ለአንተ እሰጥሃለሁ፤ [7]ስለዚህ ብት ሰግድልኝ ይህ ሁሉ የአንተ ይሆናል::”

[8]ኢየሱስም መልሶ፣ “ ‘ለጌታ ለአምላክህ ስገድ፤ እርሱንም ብቻ አምልክ’ ተብሎ ተጽፎአል” አለው::

[9]ከዚያም ወደ ኢየሩሳሌም ወስዶ በቤተ መቅደስ ጉልላት ላይ አቆመውና እንዲህ አለው፤ “የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንህ፣ እስቲ ራስ ህን ከዚህ ወደ ታች ወርውር፤ [10]ምክንያቱም እንዲህ ተብሎ ተጽፎአል፤

“ ‘ይጠብቁህ ዘንድ፣
መላእክቱን ስለ አንተ ያዛቸዋል፤
[11]እግርህም ከድንጋይ ጋር እንዳይጋጭ፣
በእጆቻቸው ወደ ላይ አንሥተው
ይይዙሃል::’ ”

[12]ኢየሱስም፣ “ ‘ጌታ ሰምላክህን አትፈታተነው’ ተብሎአል” ብሎ መለሰለት::

4፥3 ማቴ4፥3
4፥4 ዘዳ8፥3
4፥5 ማቴ24፥14
4፥6 ዮሐ12፥31፤ 14፥30፤1ዮሐ5፥19
4፥8 ዘዳ6፥13
4፥11 መዝ 91፥11:12
4፥12 ዘዳ6፥16
4፥13 ዮሐ14፥30፤ ዕብ4፥15
4፥14 ማቴ4፥12፤ 9፥26
4፥15 ማቴ4፥23
4፥16 ማቴ2፥23፤ 13፥54፤1ጢሞ4፥13
4፥18 ማር16፥15፤ ዮሐ3፥34
4፥19 ዘሌ25፥10፤ መዝ102፥20፤103፥6 ፤ኢሳ42፥7፤ 49፥8:9፤ 58፥6፤61፥1:2
4፥20 ቊ17፤ ማቴ26፥55
4፥21 ማቴ1፥22

[13]ዲያብሎስም ፈተናውን ሁሉ ከጨረሰ በኋላ ሌላ አመቺ ጊዜ እስኪያገኝ ድረስ ከእርሱ ተለየ::

## ኢየሱስ በናዝሬት ተቀባይነት ማጣቱ

[14]ኢየሱስም በመንፈስ ኀይል ወደ ገሊላ ተመለሰ፤ ዝናውም በአካባቢው ባለው አገር ሁሉ ወጣ:: [15]እርሱም በምኵራባቸው ያስተ ምር ነበር፤ ሰውም ሁሉ ያመሰግነው ነበር::

[16]ከዚያም ወዳደገበት ከተማ ወደ ናዝ ሬት መጣ፤ እንደ ልማዱም በሰንበት ወደ ምኵራብ ገባ፤ ሊያነብም ተነሥቶ ቆመ:: [17]የነቢዩ ኢሳይያስ ጥቅልል መጽሐፍም ተሰ ጠው፤ ጥቅልሉንም መጽሐፍ በተረተረው ጊዜ እንዲህ ተብሎ የተጻፈበትን ክፍል አገኘ፤

[18]“የጌታ መንፈስ በእኔ ላይ ነው፤
ለድኾች ወንጌልን እንድሰብክ፣
እርሱ ቀብቶኛልና፤
ለታሰሩት መፈታትን፣
ለታወሩትም ማየትን እንዳውጅ፣
የተጨቈኑትን ነጻ እንዳወጣ፣
[19]የተወደደችውንም የጌታን ዓመት
እንዳውጅ ልኮኛል::”

[20]ከዚያም መጽሐፉን ጠቅልሎ ለአገልጋዩ መልሶ ሰጠውና ተቀመጠ፤ በምኵራብ የነ በሩትም ሁሉ ትኵር ብለው ይመለከቱት ነበር:: [21]እርሱም፣ “ይህ በጆሮአችሁ የሰማ

---

ትም፣ በጾሙ መጨረሻ አካባቢ ሲሆን፣ ይህም ኢየሱስ በተራ በበትና በተዳከመበት ጊዜ ነው:: የሁለተኛውና የሦስተኛው ፈተናዎች ቅደም ተከተል፣ በማቴዎስና በሉቃስ ወንጌል ውስጥ ልዩነት አለው:: በተራራ ላይ ከቀረበው ፈተና በኋላ (በማቴዎስ ሦስተኛ ነው)፣ከእርሱ እንዲለይ ኢየሱስ ሰይጣንን አዝዞት ስለ ነበር፣ ማቴዎስ ፈተናውን ያቀረበው በቅደም ተከተል ሳይሆን አይቀርም (4፥10):: የወንጌል ጸሓፊዎች፣ አንድን ሁኔታ ወይም ድርጊት በአጽንዖት ለማመልከት ሲሉ፣ ለድርጊቱ ቅደም ተከተል ትኵረት ሳይሰጡ ሁኔታዎችን ወይም ድርጊቶችን አጣምረው ያቀርባሉ:: በዚህ መደምደሚያ ላይ ኢየሱስ በኢየሩሳሌም እንደ ነበር ሉቃስ መግለጹ፣ የእርሱ ትኵረት መልክዐ ምድራዊ መሆኑን ያመለክታል::

4፥3 *ከሆንህ፤* የማቴ 4፥3 ማብ ይመ:: *ይህ ድንጋይ እን ጀራ እንዲሆን እዘዝ፤* ሰይጣን ምን ጊዜም ፈተና ሲያቀርብ በሚ ማርክ ሁኔታ ነው::

4፥7 *ብትሰግድልኝ፤* ኢየሱስ የመጣው በመስቀል ላይ ሥቃይ ለመቀበል ሆኖ ሳለ (ማር 10፥45)፣ ሰይጣን ግን ከዚህ ዐላ ማው ፈቀቅ እንዲል ፈተነው፤ ስለዚህም ይህ ፈተና፣ ኢየሱስ በአ ቋራጭ መንገድ በዓለም ላይ ገዥ መሆን የሚችልበትን መንገድ የሚያመለክት ነው::

4፥9 *በቤተ መቅደስ ጉልላት፤* ከበታቹ 34 ሜትር ያህል ዝቅ ብሎ ከሚገኘው ቄድሮን ሸለቆ በደቡብ ምሥራቅ በኩል ያለው የቤተ መቅደሱ መመላለሻ በረንዳ ጫፍ፣ ወይም የቤተ መቅደሱ ጉልላት ጫፍ ሊሆን ይችላል:: *ከሆንህ፤* የማቴ 4፥3 ማብ ይመ:: *ወደታች ራስህን ወርውር፤* ኢየሱስ የአብን ታማኝ ነት እንዲፈታተንና የሰውን ሐሳብ በሚያስደንቅ ሁኔታ በመ ማረክ ዝናን ለራሱ እንዲያተርፍ ሰይጣን ፈተነው::

4፥10 *ተጽፎአል፤* ሰይጣን በመዝ 91፥11-12 ላይ ያለውን ለክፉ ዐላማው ለመጠቀም በመጥቀስ፣ ኢየሱስን ፈተነው::

*4፥12፤* ኢየሱስ በሁለቱ ፈተናዎች ጊዜ ከቅዱሳት መጻሕ ፍት በመጥቀስ መልስ እንደ ሰጠ ሁሉ፣ አሁንም ከዘዳግም በመጥቀስ መልስ ሰጠ (አግራጭ ትርጉም ይመ)::

4፥13 *አመቺ ጊዜ እስኪያገኝ፤* ኢየሱስ ባገለገለበት ዘመን ሁሉ፣ ሰይጣን እርሱን መፈተኑን አላቋረጠም (ማር 8፥33 ይመ)፤ ፈተናው ከፍተኛ ደረጃ ላይ የደረሰውም በጌቴሴማኔ ነበር::

4፥14 *በመንፈስ ኀይል፤* የቊ1 ማብ ይመ::

4፥15 *በምኵራባቸው ያስተምር ነበር፤* የማር 1፥21 ማብ ይመ::

4፥16 *ወደ ናዝሬት ከተማ መጣ፤* አገልግሎቱን ከጀመረ ከአንድ ዓመት በኋላ ሳይሆን አይቀርም (ቊ 23 ኢየሱስ አገል ግሎቱን ቀደም ብሎ የጀመረ መሆኑን ያመለክታል):: ምናልባት በዮሐ 1፥19-4፥42 ያሉት ትረካዎች ሁሉ የተፈጸሙት በሉቃ 4፥13 እና 4፥14 መካከል ሊሆን ይችላል:: *እንደ ልማዱም፤* ኢየ ሱስ ያለ ማቋረጥ በአምልኮ ጊዜ ሁሉ በመገኘት፣ ለተከታዮቹ አርአያነት አለው:: *ሊያነብ፤* ከኢሳይያስ መጽሐፍ ኢየሱስ ያነበ በው በዕብራይስጥ ቋንቋ የተጻፈውን ጥቅልል ሳይሆን አይቀርም፤ ከዚያ በኋላም እርሱ ወይም ሌላ ሰው ፍልቅቅ ሐሳቡን በዚያን ዘመን በስፋት ይጠቀሙበት በነበረው በአራማይክ ቋንቋ ተናግረ ውበት ይሆናል::

4፥17 *የነቢዩ ኢሳይያስ ጥቅልል መጽሐፍ፤* የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት የተጻፉት በጥቅልል ወረቀት ላይ ነው፣ እነዚህ ጥቅልል መጽሐፍት በምኵራብ ውስጥ በልዩ ቦታ እንዲቀመጡ የሚደረግ ሲሆን፣ ለአንባቢው የሚቀርቡት ለዚሁ ተግባር በተ መደበ ሰው አማካኝነት ነበር:: ኢየሱስ ስለ መሲሑ ያነበበው ክፍል (ኢሳ 61፥1-2)፣ እርሱ የመረጠው ወይም በዕለቱ እንዲ ነበብ የተመደበ ምንባብ ሊሆን ይችላል::

*4፥18፤* በዚህ ቍጥር ላይ ያለው ሐሳብ የሚያመለክተው፣ የእያንዳንዱን ሰው ፍላጎት የሚያሟላውን የመሲሑን የስብከትና የፈውስ አገልግሎቱን:: *ቀብቶኛል፤* በዘይት ሳይሆን (ዘፀ 30፥22-31 ይመ)፣ በመንፈስ ቅዱስ ነው::

4፥19 *የተወደደችውንም የጌታን ዓመት፤* ይህ የሚያሳየው የተወሰነ አንድን ዓመት ሳይሆን፣ የድነት ወንጌል የሚታወጅ በትን የመሢሑን ዘመን ነው:: ከኢሳ 61፥1-2 የተወሰዱት እነዚህ ቍጥሮች የኢዮቤልዩን ዓመት ያመለክታሉ:: (ዘሌ 25፥8-55)፤ ይኸውም በአምሳ ዓመት አንድ ጊዜ ባሪያዎች ነጻ የሚወጡበት፤ ዕዳ የሚሰረዝበት፤ የአያት ቅድመ አያት ንብረትም ቀድሞ ባለ ቤት ለነበረው ቤተ ሰብ የሚመለስበት ነው:: ኢሳይያስ አስቀ ድሞ የተነበየው፣ እስራኤላውያን ከሚማርኳቸው ባቢሎናውያን እጅ ነጻ እንደሚወጡ ነበር፤ ኢየሱስ ግን ከኀጢአትና ከሚያስከትለው መዘዝ ነጻ መውጣትን ዐወጀ::

4፥20 *ተቀመጠ፤* ቅዱሳት መጻሕፍትን ሲያነቡ መቆም (ቊ16)፣ ሲያስተምሩ ግን መቀመጥ የተለመደ ነበር (ማቴ 5፥1፤ 26፥55፤ ዮሐ 8፥2፤ ሐሥ 16፥13 ይመ)::

ችሁት የመጽሐፍ ቃል ዛሬ ተፈጸመ" ይላቸው ጀመር::

[22]ሁሉም ስለ እርሱ በበጎ ይናገሩ ነበር፤ ደግሞም ከአንደበቱ በሚወጣ የጸጋ ቃል እየተገረሙ፣ "ይህ የዮሴፍ ልጅ አይደለ ምን?" ይሉ ነበር::

[23]እርሱም፣"'ባለ መድኀኒት ሆይ፤ ራስ ህን ፈውስ፤ በቅፍርናሆም ስታደርግ የሰማነ ውን ነገር እዚህ በራስህ ከተማ ደግሞ አድርግ' " የሚለውን ምሳሌ እንደምትጠቅሱብኝ ጥርጥር የለውም" አላቸው::

[24]ደግሞም እንዲህ አላቸው፤ "እውነት እላችኋለሁ፤ ነቢይ በገዛ አገሩ አይከበርም:: [25]ነገር ግን እውነት እላችኋለሁ፤ ሰማይ ሦስት ዓመት ከመንፈቅ ተዘግቶ ጽኑ ራብ በምድሪቱ ሁሉ ላይ በነበረበት በኤልያስ ዘመን፣ ብዙ መበለቶች በእስራኤል ነበሩ፤ [26]ኤልያስ ከእነዚህ መካከል ወደ አንዷም አልተላከም፤ ነገር ግን በሲዶና አገር በሰራፕታ ወደ ነበረችው መበለት ተላከ:: [27]በነቢዩ በኤልሳዕ ዘመንም በእስራኤል ብዙ ለምጻሞች[*] ነበሩ፤ ነገር ግን ከሶርያዊው ከንዕማን በቀር ከእነዚያ መካካል ማንም አልነጻም::"

[28]በምኵራብ የነበሩ ሰዎች ሁሉ ይህን በሰሙ ጊዜ በቍጣ ነደዱ፤ [29]ከተቀመጡብ ትም ተነሥተው ከከተማው አስወጡት፤ ቍል ቍል ሊጥሉትም ከተማቸው ወደ ተሠራች በት ኰረብታ አፋፍ ወሰዱት፤ [30]እርሱ ግን በመካከላቸው ሰንጥቆ ሄደ::

## ኢየሱስ ርኩስ መንፈስ አስወጣ

4፥31-37 ተጓ ምብ – ማር 1፥21-28

[31]ከዚያም በገሊላ አውራጃ ወደምትገኘው ከተማ ወደ ቅፍርናሆም ወረደ፤ በዚያም በሰንበት ዕለት ሕዝቡን ያስተምር ጀመር፤ [32]የሚናገረው በሥልጣን ስለ ነበር በትምህርቱ ተደነቁ::

[33]በምኵራብም የርኩስ ጋኔን መንፈስ ያደረበት ሰው ነበረ፤ እርሱም ከፍ ባለ ድምፅ ጮኸ፣ [34]"ወዮ! የናዝሬቱ ኢየሱስ ሆይ፤ ምን የሚያገናኘን ጉዳይ አለ? የመጣኸው ልታጠፋን ነውን? አንተ ማን እንደ ሆንህ ዐውቃለሁ፤ አንተ የእግዚአብሔር ቅዱስ ነህ!" አለው::

[35]ኢየሱስም፣ "ጸጥ ብለህ ከዚህ ሰው ውጣ!" ብሎ ገሠጸው:: ጋኔኑም ሰውየውን በሕዝቡ ሁሉ ፊት ጣለውና ምንም ጕዳት ሳያደርስ በት ለቆት ወጣ::

[36]ሰዎቹም ሁሉ ተገረሙ፤ እርስ በእርሳቸውም፣ "ለመሆኑ ይህ ትምህርት ምንድን ነው? በሥልጣንና በኀይል ርኩሳን መናፍስትን ያዛል፤ እነርሱምኮ ይወጣሉ" ተባባሉ:: [37]የእርሱም ዝና በአካባቢው ወዳለው ስፍራ ሁሉ ወጣ::

## ኢየሱስ ብዙ በሽተኞችን ፈወሰ

4፥38-41 ተጓ ምብ – ማቴ 8፥14-17
4፥38-43 ተጓ ምብ - ማር 1፥29-38

[38]ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ከምኵራብ ወጥቶ ወደ ስምዖን ቤት ገባ:: የስምዖንም አማት ኀይለኛ ትኵሳት ይዞአት ታማ ነበር፤ እንዲፈውሳትም ስለ እርሷ ለመኑት:: [39] እርሱም ወደ ተኛችበት ጠጋ ብሎ በማጕንበስ ትኵሳቱን ገሠጸው፤ ትኵሳቱም ለቀቃትና ወዲያው ተነሥታ አስተናገደቻቸው::

[40]ፀሓይ መጥለቂያ ላይም፣ የተለያየ ሕመም ያደረባቸውን ሰዎች ሁሉ ወደ እርሱ አመጡ፤ እርሱም በእያንዳንዳችው ላይ እጁን ጭኖ ፈወሳቸው:: [41]አጋንንትም ደግሞ፣ "አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ነህ!" እያሉና እየጮኹ ከብዙ ሰዎች ወጡ:: እርሱ ግን ገሠጻቸው፤ ክርስቶስ[+] መሆኑንም ያውቁ ስለ ነበር፣ እንዳች እንዲናገሩ አልፈቀደላቸውም::

4፥22 ማቴ13፥54:55፤ ዮሐ 6፥42፤ 7፥15
4፥23 ቍ16፤ ማቴ2፥23፤ማር1፥21-28፤2፥1-12
4፥24 ማቴ13፥57፤ ዮሐ4፥44
4፥25 1ነገ17፥1፤ 18፥1፤ያዕ5፥17:18፤ ራእ 11፥6
4፥26 1ነገ17፥8-16፤ማቴ11፥21
4፥27 2ነገ5፥1-14
4፥29 ዘኍ15፥35፤ ሐሥ7፥58፤ ዕብ13፥12
4፥30 ዮሐ8፥59፤ 10፥39
4፥31 ቍ23፤ ማቴ4፥13
4፥32 ቍ36፣ ማቴ7፥28:29
4፥34 ቍ41፤ ማቴ8፥29፤ማር1፥24፤ ያዕ2፥19
4፥35 ቍ39:41፤ ማቴ8፥26፤ሉቃ8፥24
4፥36 ቍ32፤ ማቴ7፥28:29፤10፥1
4፥37 ቍ14፤ ማቴ9፥26
4፥39 ቍ35:41
4፥40 ማቴ4፥23፤ ማር5፥23
4፥41 ቍ35፤ማቴ 4፥3፤8፥4

[*]27 የግሪኩ ቃል የግድ ከለምጽ ጋር ብቻ የተያያዘ ሳይሆን የተለያየ የቈዳ በሽታዎች ለመግለጽ ጥቅም ላይ ይውላል
[+]41 ወይም መሲሕ

4፥23 *በራስህ ከተማ፤* በናዝሬት ማለት ነው:: ምንም እንኳ ኢየሱስ የተወለደው በቤተ ልሔም ቢሆንም፣ ያደገው ግን ገሊላ በምትገኘው በናዝሬት ከተማ ነበር (1፥26፤ 2፥39:51፤ ማቴ 2፥23):: *ቅፍርናሆም፤* የማቴ 4፥13 ማብ ይመ::

*4፥26-27፤* ኢየሱስ በትምህርቱ አይሁዳዊ ያልሆኑትን ሁለት ሰዎች እግዚአብሔር እንዴት እንደ ረዳቸው የተናገረበትን ሉቃስ መጥቀሱ (1ነገ 17፥1-15፤ 2ነገ5፥1-14)፣ ለአሕዛብ ወገን ምን ያህል ግድ ይለው እንደ ነበር ያመለክታል:: ኢየሱስ ለማስገንዘብ የፈለገው ዋና ሐሳብ፣ እስራኤላውያን የእግዚአብሔርን የድነት መልእክተኛ በተቃወሙ ጊዜ፣ እግዚአብሔር ወደ አሕዛብ እንደ ላከው፣ አሁንም እንዲሁ እርሱን አንቀበልም ስላሉ፣ እግዚአብሔር ወደ አሕዛብ እንደ ላከው ነው:: (10፥13-15፤ ሮሜ 9፥11 ይመ)::

4፥26 *ሲዶና፤* ከጢሮስ በስተ ሰሜን 32 ኪ.ሜ. ርቃ የምትገኝ ከጥንት የፊንቂአውያን ከተማዎች አንዷ ናት:: ኢየሱስም የአንዲት አሕዛብን ሴት ልጅ የፈወሰውም በዚህች ከተማ ነበር (ማቴ 15፥21-28)::

4፥28 *በቍጣ ነደዱ፤* ኢየሱስ እስራኤልን ኰንኖ፣ ለአሕዛብ ቸርነቱን በማሳየቱ ተቈጡ::

4፥30 *በመካከላቸው ሰንጥቆ ሄደ፤* ኢየሱስ በመካከላቸው ያለፈው በታምር ይሁን ወይም መንገድ እንዲለቁለት ሥልጣኑ አዞአቸው እንደ ሆነ ሉቃስ ግልጽ አላደረገም፤ ያም ሆነ ይህ ኢየሱስ ሕይወቱን አሳልፎ የሚሰጥበት ጊዜ አልደረሰም ነበር (ዮሐ 7፥30)::

*4፥32፤* የማር 1፥22 ማብ ይመ::

4፥33 *ጋኔን...ያደረበት፤* ለአረመኔዎች "ጋኔን" ማለት፣ በጎም ይሁን ክፉ፣ ሰብአዊ ያልሆነ ፍጡር ማለት ነው፤ ሉቃስ ግን ይህ "ጋኔን" ክፉ መንፈስ እንደ ሆነ ግልጽ አድርጎአል:: እንዲህ ያለው መንፈስ አእምሮን ያቃውሳል (ዮሐ 10፥20)፤ ለክፉ ሥራ ያነሣሣል (ሉቃ 8፥26-29)፤ በአካል ላይ በሽታ ያደርሳል (13፥11:16)፤ እንዲሁም በእግዚአብሔር ላይ ያሳምፃል (ራእ 16፥14)::

4፥34 *የእግዚአብሔር ቅዱስ፤* የማር 1፥24 ማብ ይመ::

4፥38 *የስምዖንም አማት፤* ጴጥሮስ ባለትዳር እንደ ነበር ያመለክታል (1ቆሮ 9፥5):: *ኀይለኛ ትኵሳት፤* ሦስቱም ተመሳሳይ ወንጌላት ስለዚህ ታምር ይናገራሉ (ማቴ 8፥14-15፤ ማር 1፥29-31)፤ የበሽታውን ሁኔታ "ኀይለኛ ትኵሳት" በማለት የገለጸው ግን፣ ሐኪሙ ሉቃስ ብቻ ነው::

4፥40 *ፀሓይ መጥለቂያ ላይ፤* የሰንበት ቀን (ቍ 31) የሚያበቃው፣ ፀሓይ ስትጠልቅ ሲሆን፣ ይህም ከምሽቱ ዐሥራ ሁለት ሰዓት ገደማ ነው:: ከዚህ ሰዓት በፊት ከሆነ ግን በሽማግሌዎች ወግ መሠረት አይሁድ ከሁለት ኪ.ሜ. የበለጠ ሊጓዙ ወይም ማንኛውንም ዐይነት ሸክም ሊሸከሙ አይገባቸውም ነበር፤ ሕመምተኛን ተሸክመው ወደ ኢየሱስ ለመውሰድ የሚችሉትም ፀሓይ ከጠለቀች በኋላ ነበር፤ ገና ፀሓይ እየጠለቀች ሳለች መንገድ መጀመራቸው፣ ሕሙማኑ እንዲፈወሱላቸው ምን ያህል ጓጉተው እንደ ነበር ያሳያል::

4፥41 ክርስቶስ መሆኑንም ያውቁ ስለ ነበር፤ የማር 1፥34 ማብ ይመ::

[42]ሲነጋም ኢየሱስ ወደ አንድ ገለልተኛ ስፍራ ሄደ፤ ሕዝቡም ይፈልጉት ነበር፤ እርሱ ወዳለበትም ቦታ መጡ፤ ከእነርሱ ተለይቶ እንዳይሄድ ሊከለክሉት ሞከሩ:: [43]እርሱ ግን፣ "ወደ ሌሎቹም ከተሞች ሄጄ የእግዚአብሔርን መንግሥት ወንጌል መስበክ ይገባኛል፤ የተላክሁት ለዚሁ ዐላማ ነውና" አላቸው:: [44]በይሁዳ ምኵራቦችም መስበኩን ቀጠለ::

## የመጀመሪያዎቹ ደቀ መዛሙርት ተጠሩ

5፥1-11 ተጓ ምብ – ማቴ 4፥18-22፤ ማር 1፥16- 20፤ ዮሐ 1፥40-42

**5** ሕዝቡ ዙሪያውን እያጨናነቁት የሚያስተምረውን የእግዚአብሔርን ቃል ሲሰሙ፣ ኢየሱስ በጌንሳሬጥ[+] አጠገብ ቆሞ ነበር፤ [2]በዚህ ጊዜ ሁለት ጀልባዎች በባሕሩ ዳርቻ ቆመው አየ፤ ዓሣ አጥማጆቹ ግን ከጀልባዎቹ ወርደው መረባቸውን ያጥቡ ነበር:: [3]ከጀልባዎቹም መካከል የስምዖን ወደ ነበረችው ገብቶ፣ ከምድር ጥቂት ፈቀቅ እንዲያደርጋት ለመነው፤ ከዚያም ጀልባዋ ላይ ተቀምጦ ሕዝቡን ያስተምር ጀመር::

[4]ንግግሩን በጨረሰ ጊዜ ስምዖንን፣ "ወደ ጥልቅ ውሃ ፈቀቅ በልና ዓሣ ለመያዝ መረባችሁን ጣሉ" አለው::

[5]ስምዖንም መልሶ፣ "መምህር ሆይ፤ ሌሊቱን ሙሉ ስንደክም አድረን ምንም አልያዝንም፤ አንተ ካልህ ግን መረቦቹን እጥላለሁ" አለው::

[6]እንደዚያም ባደረጉ ጊዜ እጅግ ብዙ ዓሣ ያዙ፤ መረባቸውም ይበጣጠስ ጀመር:: [7]በሌላ ጀልባ የነበሩት ባልንጀሮቻቸው መጥተው እንዲያግዟቸውም በምልክት ጠሯቸው፤ እነርሱም መጥተው ሁለቱን ጀልባዎች በዓሣ

4፥43 ማቴ3፥2
4፥44 ማቴ4፥23
5፥1 ማር4፥1፤ ዕብ 4፥12
5፥3 ማቴ13፥2
5፥4 ዮሐ21፥6
5፥5 ሉቃ8፥24፡45፤ 9፥33፡49፤17፥13፤ ዮሐ21፥3
5፥6 ዮሐ21፥11

[+]1 ይህ የገሊላ ባሕር ነው

4፥42 *ገለልተኛ ስፍራ፤* ከዚህ ሐረግ በተጨማሪ፣ ኢየሱስ በዚህ ስፍራ እንደ ጸለየ ማርቆስ አክሎ ጽፎአል (ማር 1፥35)::

4፥43 *የእግዚአብሔርን መንግሥት፤* ሉቃስ በወንጌሉ ለመጀመሪያ ጊዜ ይህን ሐረግ የተጠቀመው በዚህ ስፍራ ሲሆን፣ ይህም ሐረግ ከሠላሳ ጊዜ በላይ ተጽፎ ይገኛል:: በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ካሉት የዚህ ሐረግ ልዩ ልዩ ትርጕሞች መካከል የእግዚአብሔር ዘላለማዊ ንጉሥነት ይህ መንግሥት በኢየሱስ አማካይነት አሁን መገኘት፣ የመጪው መንግሥት መንፈሳዊ ገጽታና የሚመጣው መንግሥት የሚሉት ናቸው:: የማቴ 3፥2 ማብ ይመ::

*4፥44፤* ይህ ማጠቃለያ የሆነው ሐሳብ (ከቍ 14) ጀምሮ ያለው ብቻ ሳይሆን፣ የኢየሱስን የወደፊት አገልግሎት የሚያመለክት ነው:: ኢየሱስ በይሁዳ የነበረው የመጀመሪያው አገልግሎቱ በማቴ 23፥37 እና በሉቃ 13፥34 ላይ የተንጸባረቀ ቢመስልም፣ ከዮሐንስ ወንጌል በስተቀር በእነዚህ ሦስቱ ወንጌላት ውስጥ በግልጽ አልተጠቀሰም:: *በይሁዳ፤* አንዳንድ የጥንት ቅጆችና ተጓዳኝ ምንባቦች (ማቴ 4፥23፤ ማር 1፥39)፣ ይሁዳ በማለት ፈንታ ገሊላ ይላሉ (አማራጭ ትርጕሙን ይመ):: ሉቃስ ከአሕዛብ ወገን ለሆነው ሰው በመጻፉ የአይሁድ ምድር የሆነውን ፓለስቲናን በሙሉ ለማመልከት "ይሁዳ" የሚለውን ስም የተጠቀመ ይመስላል (በወንጌሉ መግቢያ ላይ፣ "የመልእክቱ ተደራስያንና ዐላማ" የሚለውን ይመ)፤ 23፥5፤ ሐሥ 10፥37 11፥1:29፤ 26፥20)::

5፥1 *በጌንሳሬጥ ባሕር፤* "ባሕር" ብሎ የጠራው ሉቃስ ብቻ ነው:: ሌሎቹ ወንጌላውያን ግን የገሊላ ባሕር ብለውታል፤ ዮሐንስ ሁለት ጊዜ የጥብርያዶስ ባሕር ብሎታል (ዮሐ 6፥1፤ 21፥1)::

5፥2 *መረባቸውን ያጥቡ ነበር፤* ዓሣ ካጠመዱ በኋላ መረቡን ማጠብና መዘርጋት፣ እንደ ገና በድጋሚ ለማጥመድ የሚደረግ ቅድመ ዝግጅት ነው::

5፥3 *ተቀምጦ፤* ለማስተማር መቀመጥ የተለመደ ነበር (የ4፥20 ማብ ይመ):: ከሕዝቡ ግፊያ ለመራቅ በጀልባ ውስጥ መሆኑ፣ በግልጽ ለመታየትና ለመደመጥ ምቹ ሁኔታን ፈጥሮለት ነበር::

5፥7 *ባልንጀሮቻቸው፤* ቍ 10 ይመ::




ቅፍርናሆም በጌታ ኢየሱስ ዘመን ዓሣ ማጥመጃ ወደብ ብቻ አልነበረችም:: ክርስቶስ ለአጠቃላይ የገሊላ አካባቢ አገልግሎቱ ማእከል ያደረጋትና ወንጌልን ከዚያ ለማሰራጨት አመቺ ሁኔታና ባሕርይ ያላት ከተማ ነበረች::

ይህም በቂ ምክንያት ነበረው:: የከተማዋ ስም ራሱ ቅፍር- ናሆም «የናሆም መንደር» (ምናልባት የነቢዩ ናሆም) የሚል ትርጕም አለው፤ ደግሞም እጅግ ብዙ ሕዝብ ለሚኖርበት አካባቢ ዋና ከተማ ከመሆኗም በላይ ሁለት ባህሎች በአኩልነት የሚስተናገዱባት ከተማ ነበረች::

በሌላ በኩል በገሊላ አውራጃ ውስጥ (በቅፍርናሆም ከነበረው ምኵራብ በተጨማሪ) ብዙ ምኵራቦች ነበሩ፤ የአይሁድ ሃይማኖት ሥርዐትም በዚህ አካባቢ ሥር ሰዶ ነበር:: በሌላ በኩል ደግሞ ለብዙ ምእተ ዓመት በአካባቢው ገኖ የነበረውና አረማዊ ባሕርይ ያለው የግሪኮች ባህልና ሃይማኖት ሥር ሰዶ ነበር:: ደግሞም ይህ የግሪኮች ሥልጣኔና አኗኗር በአካባቢው ወግ፣ አለባበስ፣ በሕንጻ አሠራር ጥበብና በፖለቲካዊ ተቋማት የራሱ የሆነ ተጽዕኖ ነበረው::

በቅርብ ጊዜ በቅፍርናሆም በተደረገው የሥነ ቅርስ ቍፋሮ፣ በአሁኑ ዘመን ቆሞ ከሚታይ አንድ የ4ኛ ምእተ ዓመት ምኵራብ ሥር ሌላ የ1ኛ ምእተ ዓመት ምኵራብ የድንጋይ ንጣፍ ተገኝቶአል:: ወደ ቤተ ክርስቲያንነት ከተለወጠውና ኋላም ሃይማኖታዊ የጕብኝት ቦታ ከሆነው ከአንድ የግል መኖሪያ ቤት አካባቢ የተገኘ ማስረጃ ይህ ቤት የስምዖን ጴጥሮስ መኖሪያ የነበረ ስለመሆኑ (ሉቃ 4:38) አንዳንድ ፍንጭ የሚሰጡ መረጃዎችን ያመለክታል::

ሞሏቸው፣ ጀልባዎቹም መስመጥ ጀመሩ።

[8]ስምዖን ጴጥሮስም ይህን ባየ ጊዜ በኢየሱስ ጕልበት ላይ ወድቆ፣ “ጌታ ሆይ፤ እኔ ኀጢአተኛ ሰው ነኝና ከእኔ ተለይ” አለው። [9]ይህንን ያለው እርሱና ከእርሱ ጋር የነበሩት በያዙት ዓሣ ብዛት ስለ ተደነቁ ነው፤ [10]ደግሞም የስምዖን ባልንጀሮች የነበሩት የዘብዴዎስ ልጆች፣ ያዕቆብና ዮሐንስም ተደነቁ።

ኢየሱስም ስምዖንን፣ “አትፍራ፤ ከእንግዲህ ሰውን የምታጠምድ ትሆናለህ” አለው። [11]እነርሱም ጀልባዎቹን ወደ ምድር ካስጠጉ በኋላ ሁሉን ትተው ተከተሉት።

## ለምጻሙ ሰው

5፥12-14 ተጓ ምብ - ማቴ 8፥2-4፤ ማር 1፥40-44

[12]ኢየሱስ ከከተሞች በአንዱ በነበረበት ጊዜ፣ አንድ ለምጽ የወረሰው* ሰው በዚያው ከተማ ነበር፤ ይህ ሰው ኢየሱስን ባየው ጊዜ በፊቱ ተደፋና፣ “ጌታ ሆይ፤ ብትፈቅድ እኮ ልታነጻኝ ትችላለህ” ብሎ ለመነው።

[13]ኢየሱስም እጁን ዘርግቶ ዳሰሰውና፣ “እፈቅዳለሁ፤ ንጻ!” አለው፤ ወዲያውም ለምጹ ጠፋለት።

[14]ኢየሱስም፣ “ይህን ለማንም አትናገር፤ ነገር ግን ሂደህ ራስህን ለካህን አሳይ፤ ለእነርሱ ምስክር እንዲሆንም ስለ መንጻትህ ሙሴ ያዘዘውን መሥዋዕት አቅርብ” ሲል አዘዘው።

[15]ይሁን እንጂ ስለ እርሱ የሚወራው ወሬ ይበልጥ እየሰፋ ሄደ፤ እጅግ ብዙ ሰዎችም እርሱ የሚናገረውን ለመስማትና ካለባቸው ደዌ ለመፈወስ ይሰበሰቡ ነበር። [16]ኢየሱስ ግን ብዙ ጊዜ ወደ ገለልተኛ ስፍራ ወጥቶ ይጸልይ ነበር።

## ኢየሱስ ሽባውን ሰው ፈወሰ

5፥18-26 ተጓ ምብ-ማቴ 9፥2-8፤ ማር 2፥3-12

[17]አንድ ቀን ኢየሱስ እያስተማረ ነበር፤ በዚያም ከገሊላና ከይሁዳ መንደሮች ሁሉ እንዲሁም ከኢየሩሳሌም የመጡ ፈሪሳውያንና የሕግ መምህራን ተቀምጠው ነበር፤ ይፈውስም ዘንድ የጌታ ኀይል ከእርሱ ጋር ነበረ። [18]በዚያን ጊዜም፣ ሰዎች አንድ ሽባ በዐልጋ ተሸክመው አመጡ፤ ኢየሱስ ፊት ለማኖርም ወደ ቤት ሊያስገቡት ሞከሩ፤ [19]ከሕዝቡም ብዛት የተነሣ ቤቱ ውስጥ ማስገባት ስላቃታቸው፣ ጣራው ላይ ወጥተው የቤቱን ክዳን በመንደል በሽተኛውን ከነዐልጋው በሕዝቡ መካከል ቀጥታ ኢየሱስ ፊት አወረዱት።

[20]ኢየሱስም እምነታቸውን አይቶ፣ “አንተ ሰው፤ ኀጢአትህ ተሰርዮልሃል” አለው።

[21]ጸሐፍትና ፈሪሳውያንም፣ “ይህ አምላክን በመዳፈር እንዲህ የሚናገር ማን ነው? ከአንዱ ከእግዚአብሔር በስተቀር ኀጢአትን ሊያስተሰርይ ማን ይችላል?” ብለው ያስቡ ጀመር።

[22]ኢየሱስም ሐሳባቸውን ስለ ተረዳ እንዲህ አላቸው፤ “ለምን በልባችሁ እንዲህ ታስባላችሁ? [23]‘ኀጢአትህ ተሰረየችልህ’ ከማለትና ‘ተነሥተህ ሂድ’ ከማለት የትኛው ይቀላል? [24]ነገር ግን ይህን ያልሁት የሰው ልጅ በምድር ላይ ኀጢአትን ለማስተስረይ ሥልጣን እንዳለው ታውቁ ዘንድ ነው።” ከዚያም ሽባውን ሰው፣ “ተነሥተህ ዐልጋህን

*12 የግሪኩ ቃል የግድ ከለምጽ ጋር ብቻ የተያያዘ ሳይሆን የተለያዩ የቈዳ በሽታዎችንም ለመግለጽ ጥቅም ላይ ይውላል።

5፥8 ዘፍ18፥27፤ ኢዮ 42፥6፤ኢሳ6፥5
5፥10 ማቴ14፥27
5፥11 ቍ28፤ ማቴ4፥19
5፥12 ማቴ8፥2
5፥14 ዘሌ14፥2-32፣ማቴ8፥4
5፥15 ማቴ9፥26
5፥16 ሉቃ3፥21
5፥17 ማቴ15፥1፤ ማር 5፥30፤ ሉቃ2፥46፤ 6፥19
5፥20 ሉቃ7፥48፡49
5፥21 ኢሳ43፥25
5፥24 ማቴ8፥20

5፥8 *ጌታ ሆይ፤... ከእኔ ተለይ፤* በአብርሃም (ዘፍ 18፥27)፣ በኢዮብና (42፥6) በኢሳይያስ (6፥5) ልምምድ እንደ ታየው ሁሉ፣ አንድ ሰው ወደ እግዚአብሔር በቀረበ ቍጥር የራሱን ኀጢአተኛነትና ዋጋ ቢስነት ይሰማዋል።

5፥11 *ሁሉን ትተው ተከተሉት፤* እነዚህ ሰዎች ከኢየሱስ ጋር ሲሆኑ፣ ይህ የመጀመሪያ ጊዜያቸው አልነበረም (ዮሐ 1፥40-42፤ 2፥1-2 ይመ)። አልፎ አልፎ የነበረውና የጠበቀ ያልነበረው ግንኙነታቸው፣ ጌታን እየተከተሉ በሄዱ ቍጥር እየጠነከረ መጣ። ይህ ሁኔታ ከማቴ 4፥18-22 እና ከማር 1፥16-20 ጋር ተመሳሳይ ቢሆንም፣ ትረካዎቹ እንደሚያመለክቱት፣ ድርጊቱ የተፈጸመው በማለዳው ክፍለ ጊዜ ተመሳሳይ ባልሆኑ ሰዓታት ነው።

*5፥12-16፤* በለምጽ በሽታ ተይዞ ስለ ነበረው ሰው መፈወስ፣ በሦስቱም ተመሳሳይ ወንጌላት ውስጥ ተገልጾአል፤ ሆኖም ድርጊቱ የተፈጸመባቸው ስፍራዎች የተለያዩ ናቸው። በማቴዎስ 8፥1-4 እንደ ተገለጠው ከተደረጉት ብዙ ታምራት መካከል አንዱ ሲሆን፣ በማርቆስ 1፥40-45 እና በሉቃስ ደግሞ በመጀመሪያው የገሊላ ጕዞ ከተከናወኑት ድርጊቶች መካከል አንዱ ሳይሆን አይቀርም።

5፥12 *ለምጽ የወረሰው፤* አማራጭ ትርጕም ይመ፤ እንዲሁም የዘሌ 13፥2 አማራጭ ትርጕም ይመ። በሽታው ምን ያህል የከፋ እንደ ሆነ የገለጸው ሉቃስ ብቻ ነው፤ ከለምጽ በሽታ ጋር በተያያዘ ሁኔታ ባይሆንም፣ የግሪኩ ቃል በሕክምና ሥነ ጽሑፍ ውስጥ ይገኛል።

5፥14 *ለማንም አትናገር፤* የማቴ 8፥4፤ 16፥20 ማብ ይመ። *ነገር ግን ሂደህ ራስህን ለካህን አሳይ፤* ጌታ ኢየሱስ ይህን በማዘዙ ሰውየው ሕግን እንዲጠብቅና ለመፈወሱ ተጨማሪ ማረጋገጫ እንዲሆን፣ ስለ ኢየሱስ አገልግሎትም ለባለሥልጣናቱ እንዲመሰክርና የመንጻትን ሥርዐትን በመፈጸም ከኅብረተሰቡ ጋር ተመልሶ እንዲዋሐድ አደረገ። ለእርሱ ምስክር እንዲሆን ለሚለው የማር 1፥44 ማብ ይመ።

5፥17 *ፈሪሳውያንና የሕግ መምህራን፤* የማቴ 2፥4፤ 3፥7 ማር 2፥16 ማብ ይመ። በገሊላ ተቃውሞ ያስነሡት እነዚህ የሃይማኖት መሪዎች ናቸው *ፈሪሳውያን፤* በሉቃስ ወንጌል ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ የተጠቀሱት እዚህ ቍጥር ላይ ነው። የስማቸው ትርጕም “የተለዩ” ማለት ሲሆን፣ ቍጥራቸውም 6000 ያህል ነበር፤ እነርሱም በመላው ፓሌስቲና ይገኙ ነበር። በምኵራብ አስተማሪዎች፣ በሕዝቡም ዘንድ የእምነት ምሳሌዎች ተደርገው የሚቈጠሩና ሕጉን ለማስከበርና ተፈጻሚነት እንዲኖረው ለማድረግ ራሳቸውን የሾሙ ሰዎች ነበሩ። ከአባቶቻቸው በዘልማድ ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን ወግና ሥርዐት፣ እንደ ቅዱሳት መጻሕፍት ሥልጣን ያለው አድርገው ይቈጥሩ ነበር (ማር 7፥8-13)። ቀደም ሲል በኢየሩሳሌም የነበሩትን የአይሁድ መሪዎች፣ ኢየሱስ ተቃውሞአል (ዮሐ 5፥ 16-18)። ስለዚህም አሁን፣ በቅፍርናሆም በአንድ ቤት ውስጥ ሳለ (ማር 2፥1-6)፣ ሊሰሙትና ሊሰልሉት መጡ። *የኦሪት የሕግ መምህራን፤* በጽሑፍና በአፍ ይነገር የነበረውን ሕግ ያጠኑ፣ የሚተረጕሙና የሚያስተምሩ “ጸሐፍት” ናቸው። ከእነዚህ መምህራን አብዛኞቹ የፈሪሳውያን ማኅበር አባላት ናቸው።

5፥19 *ጣራው፤* የማር 2፥4 ማብ ይመ። *ክዳን፤* ምናልባት የጣራውን ሊሆን ይችላል።

5፥21 *አምላክን በመዳፈር እንዲህ የሚናገር፤* የማር 2፥7 ማብ ይመ። በፈሪሳውያን አመለካከት፣ አንድ ሰው እጅግ የከፋ ኀጢአት አደረገ የሚባለው፣ በእግዚአብሔር ላይ የስድብ ቃል ሲናገር ነው (የማር 14፥64 ማብ ይመ)።

5፥23 *ከማለት የትኛው ይቀላል?* የማር 2፥9-10 ማብ ይመ።

5፥24 *ታውቁ ዘንድ፤* ኢየሱስ ለመፈወስ ያለው ኀይል፣

ተሸክመህ ወደ ቤትህ ሂድ እልሃለሁ" አለው። [25]እርሱም ወዲያው ተነሥቶ በፊታቸው ቆመ፤ ተኝቶበት የነበረውንም ተሸክሞ፣ እግዚአብሔ ርን እያመሰገነ ወደ ቤቱ ሄደ። [26]በዚህ ጊዜ ሁሉንም መገረም ያዛቸው፤ እግዚአብሔርንም እያመሰገኑ፣ "ዛሬኮ ድንቅ ነገር አየን" እያሉ በፍርሀት ተዋጡ።

## የሌዊ መጠራት

5፥27-32 ተጓ ምብ – ማቴ 9፥9-13፤ ማር 2፥14-17

[27]ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ከዚያ ወጥቶ ሄደ፤ ሌዊ የተባለ አንድ ቀረጥ ሰብሳቢም በቀ ረጥ መቀበያው ቦታ ተቀምጦ አየውና፣ "ተከተለኝ" አለው፤ [28]እርሱም ሁሉን ትቶ ተነሥቶ ተከተለው።

[29]ሌዊም ለኢየሱስ በቤቱ ትልቅ ግብዣ አደረገ፤ ብዙ ቀረጥ ሰብሳቢዎችና ሌሎች ሰዎችም ከእነርሱ ጋር በማእድ ተቀምጠው ነበር። [30]ፈሪሳውያንና ጸሐፍታቸውም "ከቀ ረጥ ሰብሳቢዎችና 'ከኀጢአተኞች' ጋር የም ትበሉትና የምትጠጡት ለምንድን ነው?" እያሉ በደቀ መዛሙርቱ ላይ አጕረመረሙ።

[31]ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "በሽተኞች እንጂ ጤነኞች ሐኪም አያስፈ ልጋቸውም፤ [32]እኔም ኀጢአተኞችን ወደ ንስሓ ልመልስ እንጂ ጻድቃንን ልጠራ አል መጣሁም።"

## ኢየሱስ ስለ ጾም ተጠየቀ

5፥33-39 ተጓ ምብ – ማቴ 9፥14-17፤ ማር 2፥18-22

[33]እነርሱም፣ "የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት አብዛኛውን ጊዜ ይጾማሉ፤ ይጸልያሉ፤ የፈሪ ሳውያን ደቀ መዛሙርትም እንደዚሁ ያደር ጋሉ፤ የአንተዎቹ ግን ዘወትር ይበላሉ፤ ይጠ ጣሉ" አሉት።

[34]ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፤ "ሙሽራው አብሮአቸው እያለ ዕድምተኞቹ እንዲጾሙ ማድረግ ይቻላልን?

[35]ነገር ግን ሙሽራው ከእነርሱ የሚወሰድ በት ቀን ይመጣል፤ በዚያን ጊዜ ይጾማሉ።"

[36]ደግሞም እንዲህ ሲል ምሳሌ ነገራቸው፤ "ከአዲስ ልብስ ላይ እራፊ ቀዶ በአሮጌ ልብስ ላይ የሚጥፍ ማንም የለም፤ እንዲህ ቢያደርግ አዲሱን ልብስ ይቀደዋል፤ አዲ ሱም እራፊ ለአሮጌው ልብስ አይስማማ ውም። [37]አዲስ የወይን ጠጅም በአሮጌ አቍማዳ ጨምሮ የሚያስቀምጥ ማንም የለም፤ እንዲህ ቢያደርግ አዲሱ የወይን ጠጅ አቍ ማዳውን ያፈነዳዋል፤ የወይን ጠጁም ይፈስ ሳል፤ አቍማዳውም ከጥቅም ውጭ ይሆናል። [38]ስለዚህ አዲስ የወይን ጠጅ በአዲስ አቍ ማዳ መጨመር አለበት፤ [39]እንግዲህ፣ አሮጌ የወይን ጠጅ ከጠጣ በኋላ፣ አዲሱን የሚሻ ማንም የለም፤ ምክንያቱም፣ 'አሮጌው የተሻለ ነው' ስለሚል ነው።"

## የሰንበት ጌታ

6፥1-11 ተጓ ምብ - ማቴ 12፥1-14 ማር 2፥23-36

6 በአንድ የሰንበት ቀን ኢየሱስ በዕርሻ መካከል ያልፍ ነበር፤ ደቀ መዛሙርቱም እሸት ቀጥፈው በእጃቸው እያሹ ይበሉ ነበር። [2]ከፈሪሳውያን መካከል አንዳንዶቹ ግን፣ "በሰ ንበት ቀን ሊደረግ ያልተፈቀደውን ለምን ታደርጋላችሁ?" አሏቸው።

[3]ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "ዳዊት በተራበ ጊዜ ከባልንጀሮቹ ጋር ያደረገውን ከቶ አላነበባችሁምን? [4]ወደ እግዚአብሔር ቤት ገብቶ ለካህናት ብቻ የተፈቀደውን ኅብስተ ገጽ ወስዶ በላ፤ አብረውት ለነበሩትም ሰጣ ቸው።" [5]ደግሞም፣ "የሰው ልጅ ለሰንበት ጌታዋ ነው" አላቸው።

[6]በሌላ ሰንበት ቀንም ወደ ምኵራብ ገብቶ ያስተምር ነበር፤ በዚያም ቀኝ እጁ የሰለለ አንድ ሰው ነበረ። [7]ጸሐፍትና ፈሪሳውያንም ሊከሱት ምክንያት በመፈለግ፣ ይፈውሰው እንደ ሆነ ለማየት ይጠባበቁት ነበር። [8]ኢየ ሱስም ሐሳባቸውን ዐውቆ እጁ የሰለለውን

5፥26 ማቴ9፥8
5፥27 ማቴ4፥19
5፥28 ቍ11፤ማቴ 4፥19
5፥29 ሉቃ15፥1
5፥30 ማቴ9፥11፤ ሐሥ23፥9
5፥32 ዮሐ3፥17
5፥33 ሉቃ7፥18፤ ዮሐ1፥35፤3፥25:26
5፥34 ዮሐ3፥29
5፥35 ሉቃ9፥22፤ 17፥22፤ዮሐ16፥5-7
6፥1 ዘዳ23፥25
6፥2 ማቴ12፥2
6፥3 ኢሳ21፥6
6፥4 ዘሌ24፥5:9
6፥5 ማቴ8፥20
6፥6 ቍ1
6፥7 ማቴ12፥2:10
6፥8 ማቴ9፥4

---

ኀጢአትን ይቅር ለማለት ያለውን ሥልጣን ያረጋግጣል።

5፥27 *ቀረጥ ሰብሳቢ፤* የ3፥12 ማብ ይመ። *በቀረጥ መቀ በያ ቦታው፤* ቀረጥ የሚሰበሰብበትን ቦታ ያመለክታል (የማር 2፥14 ማብ ይመ)።

5፥28 *ሁሉን ትቶ... ተከተለው፤* ለጥቂት ጊዜ ያህል ኢየ ሱስ በቅፍርናሆም በማገልገሉ፣ ምናልባት ሌዊ ከዚህ በፊት ያውቀው ይሆናል። (የቍ 11 ማብ ይመ)።

5፥29 *ትልቅ ግብዣ፤* ሌዊ ኢየሱስን መከተል ሲጀምር፣ በስውር ሳይሆን በግልጽ እንደ ሆነ ያመለክታል።

5፥30 *ፈሪሳውያንና... አጕረመረሙ፤* ምናልባት ደጅ ቆመው ተቃውሞአቸውን በርቀት ሳያሰሙ አይቀርም። *ከቀረጥ ሰብሳቢዎችና (ከኀጢአተኞች) ጋር የምትበሉት፤* የማቴ 2፥15 ማብ ይመ።

5፥31 *በሽተኞች እንጂ ጤነኞች ሐኪም አያስፈልጋቸውም፤* እንዲህ ሲባል፣ ፈሪሳውያን "ጤነኞች" ናቸው ለማለት ሳይሆን፣ አንድ ሰው መንፈሳዊ ፈውስ ለማግኘት አስቀድሞ ኀጢአተኛ መሆ ኑን መገንዘብ እንዳለበት ለማመልከት ነው (የማር 2፥17 ማብ ይመ)።

5፥33 *የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ... ይጾማሉ፤ ይጸልያሉ፤* መጥምቁ ዮሐንስ በምድረ በዳ ስላደገ፣ ጥቂት ምግብ፣ አንበጣና የበረሓ ማር ብቻ እየበላ መኖርን ተለማምዶ ነበር። በአገልግሎ ቱም ጠንካራ መልእክት ማቅረብና የዐላማ ጽናት ይታይ ነበር። የኢየሱስንና የመጥምቁ ዮሐንስን አገልግሎት ለማነጻጸር 7፥24-28፤ማቴ 11፥1-19 ይመ። ፈሪሳውያን የሚከተሉት የራሳቸው የሆነ የኑሮ ዘይቤ ነበራቸው (የ18፥12 ማብ ይመ)። ይሁን እንጂ ኢየሱስ ወደ ግብዣ ሄደ፤ ደቀ መዛሙርቱም በእርሱ ባገኙት ነጻነት ተደሰቱ፤ ይህ ዐይነት ነጻነት ግን፣ በፈሪሳውያን ዘንድ አይታወቅም ነበር። *ይጾማሉ፤* የማር 2፥18 ማብ ይመ። ኢየሱስ ለታይታ የሚደረገውን ቢቃወምም (ከኢሳ 58፥3-11 ጋር ያነጻጽሩ)፣ እርሱ ራሱ ግን ትክክለኛውን ጾም ጾሞአል፤ ለመንፈሳዊ ሕይ ወት ጠቀሜታ በፈቃደኝነት ላይ የተመሠረተውንም ጾም ፈቅ ዶአል (ማቴ 4፥2፤ 6፥16-18)።

5፥35፤ የማር 2፥19-20 ማብ ይመ።

5፥36 *ምሳሌ፤* የማቴ 13፥3፤ማር 4፥2 ማብ ይመ።

5፥37 *አሮጌ አቍማዳ፤* የማቴ 9፥17 ማብ ይመ።

5፥39 *አሮጌው የተሻለ ነው፤* አንዳንድ ሰዎች ልማዳዊ ከሆነ የሃይማኖት መንገዳቸው ተላቀው፣ ወደ ወንጌል እውነት ለመምጣት ምን ያህል ፈቃደኞች እንዳልሆኑ ኢየሱስ አመለከተ።

6፥1 *በዕርሻ መካከል ያልፍ ነበር፤* የማር 2፥23 ማብ ይመ።

6፥3 *ዳዊት... ያደረገውን፤* የማር 2፥25 ማብ ይመ።

6፥4 *ኅብስተ ገጽ ፤* የማቴ 12፥4 ማብ ይመ።

6፥5 *የሰው ልጅ፤* የማር 8፥31 ማብ ይመ። *ለሰንበት ጌታ፤* ኢየሱስ ሰንበትን በተመለከተ የወጡትን ሕጎቻት፣ በተለ ይም ፈሪሳውያን ሰንበት አስመልክተው የሰጡትን ትንታኔ የመ ሻር ሥልጣን አለው (ማቴ 12፥8፤ ማር 2፥27 ይመ)።

ሰው፣ “ተነሥተህ በመካካል ቁም” አለው፤ ሰውየውም ተነሥቶ ቆመ።

[9]ኢየሱስም፣ “እስቲ አንድ ነገር ልጠይቃችሁ፤ በሰንበት ቀን የተፈቀደው በጎ ማድረግ ነው ወይስ ክፉ ማድረግ? ነፍስ ማዳን ነው ወይስ ማጥፋት?” አላቸው።

[10]ደግሞም ኢየሱስ በዙሪያው ያሉትን ሁሉ ከተመለከተ በኋላ ሰውየውን፣ “እጅህን ዘርጋ” አለው። ሰውየውም እንደ ተባለው አደረገ፤ እጁም ፈጽሞ ዳነለት። [11]ሰዎቹ ግን በቍጣ ተሞሉ፤ በኢየሱስ ላይ ምን ማድረግ እንዳለባቸውም እርስ በርስ ተወያዩ።

## የዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት መመረጥ

6፥13-16 ተጓ ምብ - ማቴ 10፥2-4፤ ማር 3፥16-19፤ ሐሥ 1፥13

[12]ከእነዚያም ቀናት በአንዱ ኢየሱስ ሊጸልይ ወደ ተራራ ወጣ፤ ሌሊቱንም ሁሉ ወደ እግዚአብሔር ሲጸልይ አደረ። [13]ሲነጋም ደቀ መዛሙርቱን ጠርቶ ከእነርሱ ዐሥራ ሁለቱን መረጠ፤ እነዚህንም ሐዋርያት ብሎ ሰየማቸው፤ [14]እነርሱም፣ ጴጥሮስ ብሎ የጠራው ስምዖንና ወንድሙ እንድርያስ፣ ያዕቆብ፣ ዮሐንስ፣ ፊልጶስ፣ በርተሎሜዎስ፣ [15]ማቴዎስ፣ ቶማስ፣ የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ፣ ቀናተኛ የተባለው ስምዖን፤ [16]የያዕቆብ ልጅ ይሁዳና ኋላ አሳልፎ የሰጠው የአስቆሮቱ ይሁዳ ነበሩ።

## የቡራኬና የወዮታ ስብከት

6፥20-23 ተጓ ምብ-ማቴ 5፥3-12

[17]ኢየሱስም አብሮአቸው ከተራራው ወርዶ ደልዳላ ቦታ ላይ ቆመ፤ ከደቀ መዛሙርቱም እጅግ ብዙ ሰዎች በዚያ ነበሩ፤ ከይሁዳ ሁሉና ከኢየሩሳሌም እንዲሁም ከጢሮስና ከሲዶና ባሕር ጠረፍ የመጣ ብዙ ሕዝብም በዚያ ነበረ፣ [18]እነዚህም የመጡት ሊሰሙትና ካለባቸው ደዌ ሊፈወሱ ነበር። በርኩሳን[ገ] መናፍስት ይሠቃዩ የነበሩትም ተፈወሱ፤ [19]ኀይል ከእርሱ እየወጣ ሁሉንም ይፈውስ ስለ ነበር፣ ሰዎቹ ሁሉ እርሱን ለመንካት ይፈልጉ ነበር።

[20]ወደ ደቀ መዛሙርቱም በመመልከት እንዲህ አለ፤

“እናንት ድኾች ብፁዓን ናችሁ፤
 የእግዚአብሔር መንግሥት የእናንተ ናትና፤
[21]እናንት አሁን የምትራቡ ብፁዓን ናችሁ፤
 ኋላ ትጠግባላችሁና፤
እናንት አሁን የምታለቅሱ ብፁዓን ናችሁ፤
 ኋላ ትሥቃላችሁና፤
[22]ሰዎች ስለ ሰው ልጅ ሲጠሏችሁ፣
 ከመካከላቸው ሲለዩአችሁና ሲነቅፏችሁ፣
 ክፉ ስምም ሲሰጧችሁ ብፁዓን ናችሁ።

[23]“እነሆ፤ ወሮታችሁ በሰማይ ታላቅ ነውና፣ በዚያን ቀን ደስ ይበላችሁ ፈንድቁም፤ የቀድሞ አባቶቻቸውም በነቢያት ላይ ያደረጉት ይህንኑ ነበርና።

[24]“ነገር ግን እናንት ሀብታሞች ወዮላችሁ፤
 መጽናናታችሁን አሁኑኑ ተቀብላችኋልና።
[25]እናንት አሁን የጠገባችሁ ወዮላችሁ፤
 ኋላ ትራባላችሁና።
እናንት አሁን የምትሥቁ ወዮላችሁ፤
 ኋላ ታዝናላችሁ፤ ታለቅሳላችሁም።

6፥11 ዮሐ5፥18
6፥12 ሉቃ3፥21
6፥13 ማር6፥30
6፥15 ማቴ9፥9
6፥17 ማቴ4፥25፤ 11፥21፤ማር3፥7-8
6፥19 ማቴ9፥20፤ ማር 5፥30፤ ሉቃ5፥17
6፥20 ማቴ25፥34
6፥21 ኢሳ55፥1:2፤ 61፥2:3፤ማቴ5፥4፤ ራእ 7፥17
6፥22 ኢሳ51፥7፤ ዮሐ9፥22፤16፥2፤15፥21
6፥23 ማቴ5፥12
6፥24 ሉቃ16፥25፤ ያዕ5፥1
6፥25 ምሳ14፥13፣ ኢሳ65፥13

[ገ]18 ወይም ክፉ

6፥8 *በመካከል ቁም፤* አስቀድመው የሰውዬውን ሁኔታ እንዲያዩና ስለ ፈውሱ ምንም ዐይነት ጥርጣሬ እንዳይኖራቸው ለማድረግ ነው።

6፥9 *በሰንበት ቀን የተፈቀደው…?* ኢየሱስ ከፈሪሳውያን ሲቀርብበት የነበረውን ጥያቄና ሲሰነዘርበት የነበረውን ተቃውሞ ተቋቍሞአል፤ አሁን ደግሞ በምኵራብ ውስጥ ተሰብስቦ ለነበረው ሕዝብ ጥያቄ በማቅረብ ቀዳሚ ሆነ (የማር 3፥4 ማብ ይመ)።

6፥10 *በዙሪያው ያሉትን ሁሉ ከተመለከተ በኋላ፤* ያቀረበውን ጥያቄ ወይም ከጥያቄው በስተ ጀርባ ያለውን መልስ የሚቃወም ሰው እንዳለ ለማወቅ ኢየሱስ ፈለገ፤ ሆኖም ለመቃወም የደፈረ ማንም አልነበረም።

6፥11 *በቍጣ ተሞሉ፤* ምክንያቱም ኢየሱስ ላቀረበው ጥያቄ ምላሽ መስጠት ስላልቻሉ ነው፤ ከዚህም የተነሣም ሕይወቱን ለማጥፋት አሢረው ነበር (ዮሐ 5፥18)፤ የማር 3፥6 ማብ ይመ።

*6፥12፤* ኢየሱስ ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት የመምረጥ ዐቢይ ተግባር ከማከናወኑ በፊት፣ እንደ ልማዱ ሌሊቱን በሙሉ ሲጸልይ አደረ።

6፥13 *ደቀ መዛሙርቱን ጠርቶ፤* በ10፥1:17 ላይ እንደ ተገለጸው ወንጌልን ለማስተማር የተላኩት ሰዎች ቍጥር ሰባ ሁለት ይደርስ ስለ ነበር፣ ኢየሱስን ለመስማት ይሰበሰቡ ከነበሩት መካከል አዘውትረው የሚከተሉትና ለትምህርቱ ራሳቸውን የሰጡ ይህን ያህል ቍጥር ያላቸው ሰዎች ነበሩ ማለት ይቻላል። ከጌታ ዕርገት በኋላም፣ መቶ ሃያ ምእመናን በኢየሩሳሌም ሆነው የተሰጣቸውን ተስፋ እየተጠባበቁ እግዚአብሔርን ያመልኩ ነበር (ሐሥ 1፥15)። ዐሥራ ሁለቱንም ሐዋርያት የመረጠው ከእነዚህ ደቀ መዛሙርቱ መካከል ነው፤ “ሐዋርያ” ማለትም “ልዩ ዐደራ ተቀብሎ የተላከ” ማለት ነው (የማር 6፥30፤ የ1ቆሮ 1፥1፤ የዕብ 3፥1 ማብ ይመ)።

*6፥14-16፤* በተጨማሪ የሐዋርያት ስም ዝርዝር በማቴ 10፥2-4፣ በማር 3፥16-19፤ በሐሥ 1፥13 ተጽፎ ይገኛል፤ በማንኛውም ቦታ የሐዋርያት ስም ዝርዝር ሲጻፍ የጴጥሮስ ስም በመጀመሪያ የአስቆሮቱ ይሁዳ ደግሞ በመጨረሻ ሲጠቀስ፣ የሌሎቹ ስም ቅደም ተከተል ግን ልዩ ልዩ ነው።

6፥14 *በርተሎሜዎስ፤* በተመሳሳይ ወንጌላት ውስጥ በዚሁ ስም የሚጠራ ሲሆን፣ በዮሐንስ ወንጌል ግን ናትናኤል የተባለው ይሆናል፤ በዮሐ 1፥45 ላይ ናትናኤል ከፊልጶስ ጋር ተጠቅሶ ይገኛል።

6፥15 *ማቴዎስ፤* ሌላው ስሙ ሌዊ ነው። *የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ፤* ምናልባትም ታናሹ ያዕቆብ ተብሎ የሚጠራው ሳይሆን አይቀርም (ማር 15፥40)። *ቀናተኛ፤* የማቴ 10፥4 ማብ ይመ።

6፥16 *የያዕቆብ ልጅ ይሁዳ፤* ሌላው ስሙ ታዴዎስ ነው (ማቴ 10፥3፤ ማር 3፥18)። *የአስቆሮቱ ይሁዳ፤* ምናልባት ከይሁዳ አገር የሆነ እርሱ ብቻ ነበር፤ የተቀሩት ግን ከገሊላ የመጡ ነበሩ (የማር 3፥19 ማብ ይመ)።

6፥17 *ደልዳላ ቦታ ላይ ቆመ፤* ሜዳማ የሆነ ቦታ ሳይሆን አይቀርም፤ ይህም በዚህና በማቴ 5፥1 ላይ ካለው ዐውድ ጋር ተመሳሳይ ነው።

*6፥20-49፤* በሉቃስ ወንጌል የተጠቀሰው በደልዳላ ቦታ ላይ የቀረበው ስብከትና በማቴዎስ ወንጌል ውስጥ የሚገኘው የተራራው ስብከት (5-7) ተመሳሳይ ናቸው። ምንም እንኳን ይህ ስብከት በማቴዎስ ውስጥ ካለው በጣም አጭር ቢሆንም ሁለቱም በቡራኬ ጀምረው ስለ ቤተ ሠሪዎች በተሰጠው ትምህርት ይደመድማሉ። በማቴዎስ ወንጌል ውስጥ ከሚገኘው ስብከት አንዳንዶቹ፣ በሉቃስ ወንጌል በልዩ ልዩ ክፍሎች ይገኛሉ (ለምሳሌ 11፥2-4፤ 12፥22-31፡ 33-34)፤ ይህም ምናልባት ትምህርቱ በልዩ ልዩ ጊዜያት በተሰጡ የኢየሱስ ስብከቶች የቀረቡ መሆኑ ለማሳየት አስቦ ይሆናል።

*6፥20-23፤* ማቴ 5፥3-21 ይመ። ቡራኬው ከድኽነትና (ቍ20) ከራብ (ቍ 21) የጠለቀ ነው። ኢየሱስ የተናገረው በ “መንፈስ” ድሃ ስለ መሆንና (ማቴ 5፥3) “ጽድቅን” ስለ መራብ (ማቴ5፥6) እንደ ሆነ በማቴዎስ ወንጌል ተገልጾአል።

*6፥24-26፤* ይህ ክፍል በቍ 20-22 ከተገለጸው ጋር አንድ በአንድ ሲነጻጸር በተቃራኒነት የቀረበ ሐሳብ ነው።

[26]ሰዎች ሁሉ ስለ እናንተ መልካም
  ሲናገሩላችሁ ወዮላችሁ፤
 የቀድሞ አባቶቻቸው ለሐሰተኞች
  ነቢያት ያደረጉላቸው ይህንኑ ነበርና።

## ጠላትን መውደድ

6፥29፡30 ተጓ ምብ-ማቴ 5፥39-42

[27]“ነገር ግን ለእናንተ ለምትሰሙ እላችኋለሁ፤ ጠላቶቻችሁን ውደዱ፤ ለሚጠሏችሁም መልካም አድርጉ፤ [28]የሚረግሟችሁን መርቁ፤ ለሚበድሏችሁም ጸልዩ። [29]አንዱን ጕንጭህን ለሚመታህ ሌላውን ጕንጭህን ደግሞ ስጠው፤ መጐናጸፊያህን ለሚወስድብህ እጀ ጠባብህን አትከልክለው። [30]ለሚለምንህ ሁሉ ስጥ፤ ንብረትህን የሚወስድ እንዲመልስልህ አትጠይቀው። [31]ሰዎች እንዲያደርጉላችሁ የምትፈልጉትን እናንተም እንዲሁ አድርጉላቸው።

[32]“የሚወዷችሁን ብትወዱ ምን የተለየ ዋጋ ታገኛላችሁ? ኀጢአተኞችም እንኳ የሚወዷቸውን ይወዳሉና። [33]መልካም ላደረጉላችሁ መልካም ብታደርጉ ምን የተለየ ዋጋ ታገኛላችሁ? ኀጢአተኞችም እንኳ እንደዚያ ያደርጋሉና። [34]ብድር ይመልሳሉ ለምትሉት ብታበድሩ ምን የተለየ ዋጋ ታገኛላችሁ? ኀጢአተኞችም እንኳ ያበደሩትን ያህል መልሰው ለመቀበል ‘ለኀጢአተኞች’ ያበድራሉ። [35]ነገር ግን ጠላቶቻችሁን ውደዱ፤ መልካም አድርጉ፤ መልሳችሁ ለመቀበል ተስፋ ሳታደርጉም አበድሩ፤ በዚህም ወሮታችሁ ታላቅ ይሆናል፤ የልዑልም ልጆች ትሆናላችሁ፤ እርሱ ለማያመሰግኑና ለክፉዎች ቸር ነውና። [36]አባታችሁ ርኅሩኅ እንደ ሆነ እናንተም ርኅሩኆች ሁኑ።

## በሌሎች አለመፍረድ

6፥37-42 ተጓ ምብ – ማቴ 7፥1-5

[37]“አትፍረዱ፤ አይፈረድባችሁም፤ አትኰንኑ፤ አትኰነኑም። ይቅር በሉ፤ ይቅር ትባላላችሁ። [38]ስጡ፤ ይሰጣችኋል፤ በምትሰፍሩበት መስፈሪያ ተመልሶ ስለሚሰፈርላችሁ፣ ጫን በተደረገ፣ በተነቀነቀና በተትረፈረፈ መልካም መስፈሪያ ተሰፍሮ በዕቅፋችሁ ይሰጣችኋል።”

[39]ደግሞም ይህን ምሳሌ እንዲህ ሲል ነገራቸው፤ “ዕውር ዕውርን ሊመራ ይችላልን? ሁለቱ ተያይዘው ጕድጓድ አይገቡምን? [40]ደቀ መዝሙር ከመምህሩ አይበልጥም፤ ነገር ግን በሚገባ የተማረ ሰው ሁሉ እንደ መምህሩ ይሆናል።

[41]“በወንድምህ ዐይን ውስጥ ያለውን ጕድፍ ለምን ታያለህ? በራስህ ዐይን ውስጥ የተጋደመውን ግንድ አትመለከትምን? [42]በራስህ ዐይን ውስጥ ያለውን ግንድ ሳታይ ወንድምህን፣ ‘ወንድሜ ሆይ፤ በዐይንህ ውስጥ ያለውን ጕድፍ ላውጣልህ’ እንዴት ልትለው ትችላለህ? አንተ ግብዝ፤ በመጀመሪያ በዐይንህ ውስጥ የተጋደመውን ግንድ አውጣ፤ ከዚያ በኋላ በወንድምህ ዐይን ውስጥ ያለውን ጕድፍ ለማውጣት አጥርተህ ታያለህ።

## ዛፍና ፍሬው

6፥43፡44 ተጓ ምብ – ማቴ 7፥16፡18፡20

[43]“መልካም ዛፍ ሆኖ ሳለ መጥፎ ፍሬ የሚያፈራ የለም፤ እንዲሁም መጥፎ ዛፍ ሆኖ መልካም ፍሬ የሚያፈራ የለም። [44]ዛፍ ሁሉ በፍሬው ይታወቃል፤ ከእሾኽ የበለስ ፍሬ አይለቀምም፤ ከቀጋ ቍጥቋጦ የወይን ፍሬ አይቈረጥም። [45]መልካም ሰው በልቡ ከሞላው መልካም ነገር መልካሙን ያወጣል፤ ክፉ ሰውም በልቡ ከሞላው ክፉ ነገር ክፉውን ያወጣል፤ ሰው በልቡ ሞልቶ የተረፈውን በአፉ ይናገራልና።

## ልባምና ሰነፍ ቤት ሠሪዎች

6፥47-49 ተጓ ምብ - ማቴ 7፥24-27

[46]“እኔ የምለውን አታደርጉም፤ ታዲያ ለምን፣ ‘ጌታ ሆይ፤ ጌታ ሆይ’ ትሉኛላችሁ? [47]ወደ እኔ የሚመጣ፣ ቃሌንም ሰምቶ የሚፈጽም ሁሉ ማንን እንደሚመስል ላሳያችሁ፤ [48]ቤት ለመሥራት አጥልቆ የቈፈረና በዐለት ላይ መሠረቱን የመሠረተ ሰው ይመስላል፤ ጐርፍ በመጣ ጊዜ የውሃው ሙላት ያን ቤት ገፋው፤ በሚገባ ስለ ታነጸም ሊያንቃንቀው አልቻለም። [49]ቃሌን ሰምቶ የማይፈጽም ግን ቤቱን ያለ መሠረት በዐፈር ላይ የሠራን ሰው ይመስላል፤ የወንዝ ሙላትም ቤቱን በመታው ጊዜ ወዲያው ወደቀ፤ ክፉኛም ፈራረሰ።”

## የመቶ አለቃው እምነት

7፥1-10 ተጓ ምብ-ማቴ 8፥5-13

**7** ኢየሱስ ይህን ሁሉ በሕዝቡ ፊት ተናግሮ ከጨረሰ በኋላ ወደ ቅፍርናሆም ገባ። [2]በዚያም አንድ የመቶ አለቃ ነበረ፤ እጅግ የሚወደው አገልጋዩም ታሞበት ለሞት ተቃርቦ ነበር። [3]እርሱም ስለ ኢየሱስ በሰማ ጊዜ

6፥26 ማቴ7፥15
6፥27 ቍ35፤ማቴ 5፥44፤ሮሜ12፥20
6፥28 ማቴ5፥44
6፥30 ዘዳ15፥7፡8፡10፤ምሳ21፥26
6፥31 ማቴ7፥12
6፥32 ማቴ5፥46
6፥34 ማቴ5፥42
6፥35 ቍ27፤ ማር5፥7፤ሮሜ8፥14
6፥36 ማቴ5፥48፤ 6፥1፤ሉቃ11፥2፤ 12፥32፤ሮሜ8፥15፤ ኤፌ4፥6፤ያዕ2፥13፤1 ጴጥ1፥17፤1 ዮሐ1፥3፤3፥1
6፥37 ማቴ6፥14፤7፥1
6፥38 መዝ79፥12፤ ኢሳ65፥6፡7፤ማቴ7፥2
6፥39 ማቴ15፥14
6፥40 ዮሐ13፥16
6፥44 ማቴ12፥33
6፥45 ምሳ4፥23፤ ማቴ 12፥34፡35፤ ማር7፥20
6፥46 ሚል1፥6፤ ማቴ 7፥21፤ዮሐ13፥13፤
6፥47 ሉቃ8፥21፤ 11፥28፤ያዕ1፥22-25
7፥1 ማቴ7፥28

6፥27 *ጠላቶቻችሁን ውደዱ!* የኢየሱስ ትምህርት ማእከላዊ ሐሳብ ፍቅር ነው። ወርቃማው ሕግ (ቍ31) በመባል የሚታወቀው፣ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ አንዳንድ ጊዜ በአሉታዊ መልክ የሚጠቀስ ቢሆንም፣ ኢየሱስ ያስተማረው ሌሎች ሰዎችን እንዳንጎዳ ብቻ ሳይሆን ይልቁንም ሰዎች ሁሉ ጠላቶቻችን እንኳ ቢሆኑ እንድንወድ ነው።

6፥29 *ሌላውን… ስጠው!* የመበቀል ዝንባሌ ሊኖረን እንደ ማይገባ ያመለክታል።

6፥36 *አባታችሁ ርኅሩኅ እንደ ሆነ!* የእግዚአብሔር ፍጹምነት አርአያችንና የምንከተለው ግባችን መሆን አለበት (ማቴ 5፥48 ይመ)

6፥37 *አትፍረዱ!* ኢየሱስ ያወገዘው ቅንነት የጐደለውንና በትዕቢትም በሌሎች ላይ የሚሰጠውን ፍርድ እንጂ፣ የእርሱ ተከታዮች ክፉውን ከደጉ እንዳይለዩ አይደለም (ከቍ43-45 ጋር ያነጻጽሩ)።

6፥38 *በዕቅፋችሁ ይሰጣችኋል!* እግዚአብሔር ለሌሎች የሰጠውን ስጦታ መዝኖ፣ በምላሹ በራሱ መስፈሪያ ሰፍሮ እንደሚሰጠን ያመለክታል፣ የምንቀበለው በረከትና ሽልማት የሚለካው፣ ለሌሎች ባሳየነው ልግስና መጠን ነው (2ቆሮ 9፥6)።

6፥41 *ጕድፍ… ግንድ!* የገዛ ራሳችንን ስሕተት ዘንግተን፣ በሌላ ሰው ላይ መፍረዳችን ምን ያህል ሞኝነትና ግብዝነት እንደ ሆነ ለማሳየት፣ ኢየሱስ ትምህርቱን ያስተላለፈበት ዘይቤአዊ አነጋገር ነው።

7፥2 *የመቶ አለቃ… አገልጋዩም!* ይህ የመቶ አለቃ፣ በሮም መንግሥት ሥርዐት መሠረት የተደራጀው መቶ ሰዎችን በአባልነት ባቀፈው የሄሮድስ አንቲጳስ ሰራዊት ውስጥ አባል ሊሆን ይችላል። በአዲስ ኪዳን ውስጥ የተጠቀሱት የሮም መቶ አለ

አገልጋዩን እንዲፈውስለት ይለምኑት ዘንድ አንዳንድ የአይሁድ ሽማግሌዎችን ላከበት። 4መልእክተኞቹም ወደ ኢየሱስ በመጡ ጊዜ እንዲህ ብለው አጥብቀው ለመኑት፤ "ይህን ልታደርግለት ይገባዋል፤ 5ምክንያ ቱም ይህ ሰው ሕዝባችንን ይወዳል፤ ምኵራባችንንም ያሠራልን እርሱ ነው።" 6ኢየሱስም ከእ ነርሱ ጋር ሄደ።

እርሱም ወደ ቤቱ በተቃረበ ጊዜ፣ የመቶ አለቃው ወዳጆቹን ልኮ እንዲህ አለው፤ "ጌታ ሆይ፤ ከቤቴ ጣራ በታች ልትገባ የሚገባኝ ሰው አይደለሁምና አትድከም፤ 7ከዚህም የተነሣ በአንተ ፊት ለመቅረብ እንኳ እንደ ሚገባኝ ራሴን አልቈጠርሁም፤ ብቻ አንድ ቃል ተናገር፤ አገልጋዬ ይፈወሳል። 8እኔ ራሴ የበላይ አለቃ አለኝ፤ ከበታቼም የማዛ ቸው ወታደሮች አሉኝ፤ አንዱን፣ 'ሂድ' ስለው ይሄዳል፤ ሌላውን፣ 'ና' ስለው ይመ ጣል፤ አገልጋዬንም፣ 'ይህን አድርግ' ስለው የታዘዘውን ያደርጋል።"

9ኢየሱስም ይህን ሲሰማ በእርሱ ተደነቀ፤ ዘወር ብሎም ይከተለው ለነበረው ሕዝብ፣ "እላችኋለሁ፤ እንዲህ ያለ ትልቅ እምነት በእስራኤል እንኳ አላገኘሁም" አላቸው። 10የተላኩት ሰዎችም ወደቤት በተመለሱ ጊዜ፣ አገልጋዩን ድኖ አገኙት።

## ኢየሱስ የመበለቲቱን ልጅ ከሞት አስነሣው

7፥11-16 ማመ1- ነገ 17፥17-24፤ 2ነገ 4፥32-37፤ ማር 5፥21-24፡35-43፤ ዮሐ 11፥1-44

11ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ብዙ ሳይቈይ፣ ናይን ወደምትባል ከተማ ሄደ፤ ደቀ መዛሙርቱና ብዙ ሕዝብም አብረውት ሄዱ። 12ወደ ከተ ማዋ መግቢያ በር ሲደርስም፣ እነሆ፤ ሰዎች የአንድ ሰው አስከሬን ተሸክመው ከከተማዋ ወጡ፤ ሟቹም ለእናቱ አንድ ልጅ ብቻ ነበር፤ እናቱም መበለት ነበረች፤ ብዙ የከተ ማውም ሕዝብ ከእርሷ ጋር ነበረ። 13ጌታም ባያት ጊዜ ራራላትና፣ "አይዞሽ፤ አታልቅሺ" አላት።

14ቀረብ ብሎም ቃሬዛውን ነካ፤ የተሸ ከሙትም ሰዎች ቀጥ ብለው ቆሙ፤ ኢየሱ ስም፣ "አንተ ጐበዝ፤ ተነሥ እልሃለሁ!" አለው። 15የሞተውም ሰው ቀና ብሎ ተቀ መጠ፤ መናገርም ጀመረ። ኢየሱስም ወስዶ ለእናቱ ሰጣት።

16ሁሉም በፍርሀት ተውጠው እግዚአብሔርን እያ መሰገኑ፣ "ታላቅ ነቢይ በመካከላችን ተነሥቶ አል"፤ "እግዚአብሔርም ሕዝቡን ጐብኝቶአል" አሉ። 17ይህም የኢየሱስ ዝና በመላው ይሁዳና' በአካባ ቢው ባለው አገር ሁሉ ወጣ።

## ኢየሱስና መጥምቁ ዮሐንስ

7፥18-35 ተጓ ምብ - ማቴ 11፥2-19

18የመጥምቁ ዮሐንስ ደቀ መዛሙርትም ይህንን ሁሉ ለዮሐንስ ነገሩት። እርሱም ከመካከላቸው ሁለቱን ጠርቶ፣ 19"ይመጣል የተባለልህ አንተ ነህ? ወይስ ሌላ እንጠ ብቅ? በሉት" ብሎ ወደ ጌታ ላከቻው።

20ሰዎቹም ወደ ኢየሱስ መጥተው፣ "መጥ ምቁ ዮሐንስ፣ 'ይመጣል የተባለልህ አንተ ነህ? ወይስ ሌላ እንጠብቅ? ብሎ ወደ አንተ ልኮናል' አሉት።

21በዚያኑ ጊዜ ኢየሱስ ብዙ ሰዎችን ከበ ሽታ፣ ከደዌና ከርኩሳን መናፍስት ፈወሳ ቸው፤ የብዙ ዐይነ ስውራንንም ዐይን አበራ። 22ከዮሐንስ ተልከው የመጡትንም እንዲህ አላቸው፤ "ሂዱችሁ ያያችሁትንና የሰማችሁ ትን ለዮሐንስ ንገሩት፤ ዐይነ ስውራን ያያሉ፤ ዐንካሶች በትክክል ይራመዳሉ፤ ለምጻሞች' ነጽተዋል፤ ደንቈሮዎች ይሰማሉ፤ ሙታን ተነሥተዋል፤ ለድኾችም ወንጌል ይሰበካል፤ 23በእኔ የማይሰናከል ሰው ሁሉ የተባረከ ነው።"

7፥7 መዝ107፥20
7፥13 ቍ19፤ሉቃ 10፥1፤13፥15፤17፥5፤ 22፥61፤24፥34፤ ዮሐ11፥2
7፥14 ማቴ9፥25፤ ማር 1፥31፤ሉቃ 8፥54፤ዮሐ11፥43፤ ሐሥ9፥40
7፥16 ቍ39፤ ማቴ9፥8፤21፥11፤ ሉቃ1፥65፤1፥68
7፥17 ማቴ9፥26
7፥18 ማቴ3፥1፤ ሉቃ5፥33
7፥21 ማቴ4፥23
7፥22 ኢሳ29፥18፡ 19፤35፥5፡6፤ 61፥1፡2፤ሉቃ4፥18

'17 ወይም *በአይሁድ ምድር*
'22 የግሪኩ ቃል የግድ ከለምጽ ጋር ብቻ የተያያዘ ሳይሆን የተለያዩ የቈዳ በሽታዎች ለመግለጽ ጥቅም ላይ ይውላል

ቆች፣ የሚደነቅ ባሕርይ አሳይተዋል (ለምሳሌ ሐሥ 10፥2፤ 23፥17-18፤ 27፥43)። ይህ የመቶ አለቃ ከአሕዛብ ወገን ቢሆ ንም፣ ለአገልጋዩ ከልብ መጨነቁ ስለ እርሱ መልካም በሚናገሩ በአይሁዳውያን ዘንድ ተደናቂነትን አትርፎአል (ቍ 5፡9 ይመ)።

7፥3 *የአይሁድ ሽማግሌዎችን፤* የምኵራብ አለቆች ባይሆኑም፣ በማኅበረ ሰቡ ዘንድ ግን እጅግ የተከበሩ ናቸው። እነርሱም ወደ ኢየ ሱስ መጥተው ለመቶ አለቃው ለመለመን ፈቃደኞች ነበሩ። ማቴ ዎስ ወንጌል ውስጥ (ማቴ 8፥5-13) ኢየሱስን የለመነው መቶ አለ ቃው ራሱ ነው፤ በሉቃስ ወንጌል ግን ልመናውን ያቀረበው በወዳ ጆቹ አማካይነት ነው (የማቴ 8፥5 ማብ ይመ)።

7፥6 *ከቤቴ ጣራ በታች ልትገባ የሚገባኝ ሰው አይደለ ሁም፤* የማቴ 8፥8 ማብ ይመ።

7፥9 *ተደነቀ፤* ስለ ኢየሱስ መደነቅ የተነገረው ሁለት ጊዜ ብቻ ነው፤ ይኸውም እዚህ ቦታ ላይ በመቶ አለቃው እምነት ምክንያት ሲሆን፣ በናዝሬት ግን እምነት ስለሌላቸው ነበር (ማር 6፥6)።

7፥14 *ቃሬዛውን፤* የአይሁድ ልማድና ሞቶ የነበረው ሰው ለኢየሱስ ትእዛዝ ምላሽ በመስጠት ከተጋደመበት ተነሥቶ መቀ መጡ እንደሚያመለክተው፣ ይህን ሰው የተሸከሙበት ቃሬዛ ከላይ በኩል ክፍት ነበር። ኢየሱስ የሞቱ ሰዎችን ካስነሣባቸው ሦስት ሁኔታዎች ይሄኛው የመጀመሪያው ሲሆን፣ የተቀሩት ደግሞ የኢያኢሮስ ሴት ልጅና (8፥40-56) አልዓዛር ናቸው (ዮሐ 11፥38-44)።

7፥18 *የ... ዮሐንስ ደቀ መዛሙርትም፤* መጥምቁ ዮሐንስ ቢታሰ ርም፣ ደቀ መዛሙርቱ ከእርሱ ጋር የነበራቸውን ግንኙነት ሳያቋ ርጡ፣ ጀምሮት የነበረውንም አገልግሎት ቀጥለው ነበር።

7፥19 *ሌላ እንጠብቅ?* ዮሐንስ ስለ ክርስቶስ መምጣት ያበ ሠረ ቢሆንም፣ አሁን ግን ዮሐንስ ራሱ በወራት ያህል በእስር ቤት በመማቀቅ ላይ ይገኛል፤ የኢየሱስ ሥራም ዮሐንስ የጠበቀ ውን ዐይነት ውጤት አላስገኘለትም። የመጥምቁ ዮሐንስ ተስፋ መቁረጥ በማንም ላይ ሊደርስ የሚችል ነው። ኢየሱስ መሲሑ ለመሆኑ እንደ ገና ማረጋገጫ ከመፈለጉም በላይ ተጨማሪ ታም ራዊ ድርጊት እንዲያደርግም ለማበረታታት ሳይሆን አይቀርም።

7፥22 *ያያችሁትንና የሰማችሁትን ለዮሐንስ ንገሩት፤* ወደ ፈወሳቸውና ከሙታን በማስነሣት ታምር ወደሠራላቸው ሰዎች በማመልከት ኢየሱስ መልስ ሰጣቸው፤ በዚህም፣ መሲሑ ሲመጣ ይፈጽማቸዋል ተብለው አስቀድሞ በትንቢት የተነገሩትን ጉልሕ ማስረጃዎችን እንጂ፣ የተስፋ ቃል አልሰጣቸውም። *ለድኾችም ወንጌል ይሰበካል፤* ኢየሱስ ያከናወናቸውን ሥራዎች መለስ ብሎ ሲቃኝ፣ ቀላል ከሆኑት ጀምሮ ከባድ እስከሆኑት ድርጊቶች በቀ ደም ተከተል ተናግረው ሙታን መነሣታቸውና ወንጌል ለድኾች መሰበኩ መደምደሚያ በማድረግ ነው። በቅዱሳን መጻሕፍት ስለ መሲሑ የተተነበዩትንም፣ በዚህ መንገድ ኢየሱስ፣ ዮሐንስን አስ ታወሰው (ኢሳ 29፥18-21፤ 35፥5-6፤ 61፥1፤ ይመ እንዲሁም ሉቃ 4፥18 ይመ)።

7፥23 *የማይሰናከል ሰው፤* ኢየሱስ፣ ተስፋ መቁረጥና ጥርጣሬ ዮሐንስን እንዲይዘው አልፈለገም።

[24]የዮሐንስ መልእክተኞች ከሄዱ በኋላ፣ ኢየሱስ ለሕዝቡ ስለ ዮሐንስ ይናገር ጀመር፤ እንዲህም አለ፤ “ወደ በረሓ የወጣችሁት ምን ልታዩ ነው? ነፋስ የሚያወዛውዘውን ሸምበቆ? [25]እኮ! ምን ልታዩ ወጣችሁ? ያማረ ልብስ የለበሰውን ሰው ነውን? ባማረ ልብስ የሚሽሞነሞኑና በድሎት የሚኖሩ በቤተ መንግሥት አሉላችሁ። [26]እኮ! ምን ልታዩ ወጣችሁ? ነቢይን ለማየት ይሆን? አዎን፣ እላችኋለሁ፤ ለማየት የወጣችሁት ከነቢይም የሚበልጠውን ነው። [27]እንዲህ ተብሎ የተጻፈለትም እርሱ ነው፤

“ ‘መንገድህን በፊትህ የሚያስተካክል፣
 መልእክተኛዬን ከአንተ አስቀድሜ እልካለሁ።’

[28]እላችኋለሁ፤ ከሴት ከተወለዱት መካከል ከዮሐንስ የሚበልጥ የለም፤ በእግዚአብሔር መንግሥት ግን ከሁሉ የሚያንሰው ይበልጠዋል።”

[29]ቀረጥ ሰብሳቢዎች እንኳ ሳይቀሩ፣ ይህን የኢየሱስን ቃል የሰሙ ሁሉ፣ በዮሐንስ እጅ በመጠመቅ ለእግዚአብሔር ተገቢውን ክብር ሰጡት፤ [30]ፈሪሳውያንና ሕግ ዐዋቂዎች ግን በዮሐንስ እጅ ባለ መጠመቃቸው፣ እግዚአብሔር ለእነርሱ ያለውን ዐላማ አቃለሉ።

[31]ኢየሱስ በመቀጠል እንዲህ አለ፤ “እንግዲህ የዚህን ትውልድ ሰዎች በምን ልመስላቸው? ምንስ ይመስላሉ? [32]በገበያ ቦታ ተቀምጠው እርስ በርሳቸው እየተጠራሩ እንዲህ የሚባባሉ ልጆችን ይመስላሉ፤

“ ‘ዋሽንት ነፋንላችሁ፤
 አልጨፈራችሁም፤
ሙሾ አወረድንላችሁ፤
 አላለቀሳችሁም።’

[33]ምክንያቱም መጥምቁ ዮሐንስ እህል ሳይበላና የወይን ጠጅ ሳይጠጣ ቢመጣ፣ ጋኔን አለበት አላችሁት፤ [34]የሰው ልጅ ደግሞ እየበላና እየጠጣ ቢመጣ፣ በላተኛና ጠጪ፣ የቀረጥ ሰብሳቢዎችና ‘የኀጢአተኞች’ ወዳጅ አላችሁት። [35]እንግዲህ የጥበብ ትክክለኛነት በልጆቿ ሁሉ ዘንድ ተረጋገጠ።”

7፥26 ማቴ 11፥9
7፥27 ሚል 3፥1፤ ማቴ 11፥10፤ ማር 1፥2
7፥28 ማቴ 3፥2
7፥29 ማቴ 21፥32፤ ማር 1፥5፤ ሉቃ 3፥12
7፥30 ማቴ 22፥35
7፥33 ሉቃ 1፥15
7፥34 ሉቃ 5፥29፡30፤ 15፥1፡2

## አንዲት ሴት ኢየሱስን ሽቶ ቀባች

7፥37-39 ማመ – ማቴ 26፥6-13፤ ማር 14፥3-9፤ ዮሐ 12፥1-8
7፥14፡42 ማመ - ማቴ 18፥23-34

[36]ከዚህ በኋላ ከፈሪሳውያን አንዱ ምግብ አብሮት እንዲበላ ኢየሱስን ጋበዘው፤ እርሱም ወደ ፈሪሳዊው ቤት ሄዶ በማእድ ተቀመጠ። [37]በዚያ ከተማ የምትኖር አንዲት ኀጢአተኛ ሴት፣ ኢየሱስ በፈሪሳዊው ቤት በማእድ መቀመጡን በሰማች ጊዜ አንድ የአልባስጥሮስ ብልቃጥ ሽቶ ይዛ መጣች፤ [38]ከበስተ ኋላው እግሩ አጠገብ ቆማ እያለቀሰች እግሩን በእንባዋ ታርስ፣ በራሷም ጠጕር ታብሰው ጀመር፤ እግሩንም እየሳመች ሽቱውን ቀባችው።

[39]የጋበዘውም ፈሪሳዊ ይህን ባየ ጊዜ፣ “ይህ ሰው ነቢይ ቢሆን ኖሮ፣ የነካችው ሴት ማን እንደ ሆነች፣ ደግሞም ምን ዐይነት ሰው እንደ ሆነች ባወቀ ነበር፤ ኀጢአተኛ ናትና” ብሎ በልቡ አሰበ።

[40]ኢየሱስም፣ “ስምዖን ሆይ፤ የምነግርህ ነገር አለኝ” አለው።

እርሱም፣ “መምህር ሆይ፤ ንገረኝ” አለው።

[41]ኢየሱስም እንዲህ አለው፤ “ከአንድ አበዳሪ ገንዘብ የተበደሩ ሁለት ሰዎች ነበሩ፤ አንደኛው አምስት መቶ ዲናር፣ ሁለተኛው ደግሞ አምሳ ዲናር ነበረበት። [42]የሚከፍሉትም ቢያጡ ዕዳቸውን ለሁለቱም ተወላቸው። እንግዲህ ከሁለቱ አበዳሪውን አብልጦ የሚወደው የትኛው ነው?”

[43]ስምዖንም፣ “ብዙው ዕዳ የተተወለት ይመስለኛል” ሲል መለሰ።

ኢየሱስም፣ “ትክክል ፈርደሃል” አለው።

[44]ወደ ሴቲቱም ዞሮ ብሎ ስምዖንን እን

7፥39 ቍ 16፤ ማቴ 21፥11
7፥44 ዘፍ 18፥4፤ 19፥2፤ 43፥24፤ መሳ 19፥21፤ ዮሐ 13፥4-14፤ 1ጢሞ 5፥10

7፥24 *የወጣችሁት ምን ልታዩ ነው?* ዮሐንስ እውነተኛ ነቢይ እንጂ፣ በሰው ሐሳብ የሚመራ ደካማ መልክተኛ አልነበረም።

7፥26 *ከነቢይም የሚበልጠውን፤* ዮሐንስ ለመሲሑ መንገድ ለማዘጋጀት የተላከ ልዩ ነቢይ ነበር።

7፥28 *በእግዚአብሔር መንግሥት... ከሁሉ የሚያንሰው፤* የማቴ 11፥11 ማብ ይመ።

7፥30 *ሕግ ዐዋቂዎች፤* ሉቃስ፣ “ጸሐፍትን” (የኦሪት ሕግ መምህራን) ለይቶ ለመጥራት የተጠቀመበት ስያሜ ነው (10፥25፡37፤ 11፥45-46፡52፤ 14፥3፤ ይመ እንዲሁም ማቴ 22፥35 ይመ)። *እግዚአብሔር... ያለውን ዐላማ አቃለሉ፤* ቀረጥ ሰብሳቢዎች ንስሓ ለመግባት ፈቃደኞች መሆናቸውን በዮሐንስ በመጠመቅ ሲያሳዩ ፈሪሳውያን ግን የእግዚአብሔርን መልእክት መቃወማቸውን ያሳዩት ባለ መጠመቅ ነው።

7፥32 *በገበያ ቦታ ተቀምጠው... ልጆችን ይመስላሉ፤* ለፈንጠዚያ፣ ጨዋታም ለመጫወት ሆነ ለሐዘን እንጕርጕሮ እንቢተኞች እንደ ሆኑ ልጆች፣ በወቅቱ የነበሩት ሰዎች በተለያየ ምክንያት ዮሐንስንም ሆነ ኢየሱስን ለመቀበል ፈቃደኞች አልነበሩም። ዮሐንስ ጥብቅ የሆነውን ሕግ ሲከተል ከእርሱ ጋር አልተባበሩም፤ እንዲሁም ኢየሱስ ልዩነት ሳያደርግ ማንኛውንም ሰው ሲቀበል እያዩ ይህንኑ በጎ ነው ብለው አልተቀበሉም።

7፥34 *የቀረጥ ሰብሳቢዎችና ‘የኀጢአተኞች’ ወዳጅ፤* ኢየሱስ የሃይማኖት ሰዎች ከሆኑትና በኅብረተ ሰቡ ዘንድ ከተናቁት ጋር አብሮ በልቶአል፤ ተነጋግሮአልም። ቀረጥ ሰብሳቢ የነበረውንም እንኳ፣ ሐዋርያ እንዲሆን ጠርቶታል (5፥27-32)።

7፥35 *የጥበብ ትክክለኛነት በልጆችዋ ሁሉ ዘንድ ተረጋገጠ፤* ማስተዋል የጎደላቸው ነቃፊዎች ከሚያቀርቡት ተቃውሞ በተቃራኒ፣ በመንፈስ ጠቢባን የሆኑ ሰዎች በመጥምቁ ዮሐንስና በኢየሱስ አገልግሎቶች መካከል ልዩነት ቢኖርም፣ ሁለቱም ከእግዚአብሔር እንደ ነበሩ መለየት ችለዋል። የማቴ 11፥19 ማብ ይመ።

7፥36 *ከፈሪሳውያን አንዱ፤* የ5፥17 ማብ ይመ። ምናልባት ዐላማው ከኢየሱስ ከመማር ይልቅ፣ ኢየሱስን ለማጥመድ ሳይሆን አይቀርም።

7፥37 *አንዲት ኀጢአተኛ ሴት፤* ዝሙት አዳሪ የነበረች ስትሆን፣ ኢየሱስ ሲሰብክ የሰማችውና ንስሓ በመግባት በአዲስ ሕይወት ለመመላለስ ቁርጥ ሐሳብ ያደረገች ናት። የመጣችውም ይቅርታ እንደምታገኝ በሚረዳት፣ ፍቅርዋን ለመግለጽና ምስጋና ለማቅረብ ነው። *የአልባስጥሮስ ብልቃጥ፤* ረጅም ዐንገትና ክብ ቅርጽ ያለው ጠርሙስ ነው።

7፥38 *ከበስተ ኋላው እግሩ አጠገብ ቆማ፤* በምግብ አበላል ልማዳቸው መሠረት፣ ኢየሱስ መደብ ላይ በመሆን ጋደም ብሎ ትራሱ ተደግፎ ፊቱ ወደ ማዕድ ስለ ነበር፣ ሴቲቱ እርሱን ሳታስቸግር ከበስተ ኋላው በጠጕርዋ እግሩን ታብስ ነበር። *ሽቱውን ቀባችው፤* ምናልባት ሴቲቱ በመጀመሪያ ለመቀባት ያሰበችው፣ የኢየሱስን ራስ ሊሆን ይችላል፤ በዚህ ፈንታ ግን፣ እግሩን ቀባች። ለስቅለቱ አንድ ሳምንት ሲቀረው፣ በተመሳሳይ ሁኔታ የቢታንያዋ ማርያምም የጌታን እግር ሽቱ ቀብታለች (ዮሐ 12፥3)።

7፥41 *አምስት መቶ ዲናር፤* አግራጭ ትርጕም ይመ።

ዲህ አለው፤ "ይህቺን ሴት ታያታለህን? እኔ ወደ ቤትህ ገባሁ፤ አንተ ለእግሬ ውሃ እንኳ አላቀረብህልኝም፤ እርሷ ግን እግሬን በእንባዋ እያራሰች በጠጕሯ አበሰች:: 45 አንተ ከቶ አልሳምኸኝም፤ እርሷ ግን ከገባሁ ጀምራ እግሬን ከመሳም አላቋረጠችም:: 46 አንተ ራሴን ዘይት አልቀባህም፤ እርሷ ግን እግ ሬን ሽቶ ቀባች:: 47 ስለዚህ እልሃለሁ፤ እጅግ ወዳለችና ብዙው ኀጢአቷ ተሰርዮላታል፤ በትንሹ የተሰረየለት ግን የሚወደው በት ንሹ ነው::"

48 ኢየሱስም ሴቲቱን፣ "ኀጢአትሽ ተሰ ርዮልሻል" አላት::

49 አብረውት በማእድ ተቀምጠው የነበሩ እንግዶችም፣ "ይህ ኀጢአትን እንኳ የሚ ያስተሰርይ እርሱ ማን ነው?" ብለው በልባ ቸው አሰቡ::

50 ኢየሱስም ሴቲቱን፣ "እምነትሽ አድኖ ሻል፤ በሰላም ሂጂ" አላት::

**የዘሪው ምሳሌ**

8፥4-15 ተጓ ምብ – ማቴ 13፥2-23፤ ማር 4፥1-20

8 ከዚህ በኋላ ኢየሱስ የእግዚአብሔርን መንግሥት የምሥራች ቃል እየሰበከ በየከተማውና በየመንደሩ አለፈ:: ዐሥራ ሁለቱም ከእርሱ ጋር ነበሩ፤ 2 እንዲሁም ከር ኩሳን መናፍስትና ከደዌ የተፈወሱ አንዳንድ ሴቶች አብረውት ነበሩ፤ እነርሱም ሰባት አጋንንት የወጡላት መግደላዊት የተባለችው ማርያም፣ 3 የሄሮድስ ቤት ኀላፊ የነበረው የኩዛ ሚስት ዮሐና፣ ሶስና፣ ደግሞም ሌሎች ብዙዎች ነበሩ፤ እነዚህም በግል ንብረታቸው የሚያገለግሉት ነበሩ::

4 ብዙ ሕዝብ በአንድነት ተሰብስቦ ሳለ፣ ደግሞም ሰዎች ከተለያዩ ከተሞች ወደ እርሱ በሚጐርፉበት ጊዜ፣ ይህን ምሳሌ እንዲህ ሲል ነገራቸው፤ 5 "አንድ ዐራሽ ዘሩን ሊዘራ ወጣ፤ ሲዘራም፣ አንዳንዱ ዘር መን ገድ ዳር፤ ወደቀ በእግርም ተረጋገጠ፤ የሰማይ ወፎችም በሉት:: 6 አንዳንዱም ዘር በድንጋያማ ቦታ ላይ ወደቀ፤ እንደ በቀለም ርጥበት አልነበረውምና ደረቀ:: 7 ሌላው ዘር ደግሞ እሾኽ መካከል ወደቀ፤ እሾኹም አብሮት አደገና አንቆ አስቀረው:: 8 ሌላውም ዘር በመልካም መሬት ላይ ወደቀ፤ በበቀለም ጊዜ መቶ ዕጥፍም አፈራ::"

ይህን ብሎ ሲያበቃም ድምፁን ከፍ አድ ርጎ፣ "ሰሚ ጆሮ ያለው ይስማ" አለ::

9 ደቀ መዛሙርቱም የዚህን ምሳሌ ትር ጕም ጠየቁት:: 10 እርሱም እንዲህ አለ፤ "የእግዚአብሔርን መንግሥት ምስጢር ማወቅ ለእናንተ ተሰጥቶአል፤ ለሌሎች ግን በምሳሌ እናገራለሁ፤ ይኸውም፣

" 'እያዩ ልብ እንዳይሉ፣
እየሰሙም እንዳያስተውሉ ነው::'

11 "እንግዲህ የምሳሌው ትርጕም ይህ ነው፤ ዘር የተባለው የእግዚአብሔር ቃል ነው:: 12 በመ ንገድ ዳር የወደቀው ቃሉን የሚሰሙ፣ ነገር ግን አምነው እንዳይድኑ ዲያብሎስ መጥቶ

7፥45 ሉቃ22፥47፡48፤ሮሜ16፥16
7፥46 መዝ23፥5፤ መክ9፥8
7፥48 ማቴ9፥2
7፥50 ማቴ9፥22፤ ሐሥ15፥33
8፥1 ማቴ4፥23
8፥2 ማቴ27፥55፡56
8፥3 ማቴ14፥1
8፥8 ማቴ11፥15
8፥10 ኢሳ6፥9፤ ማቴ13፥11፡13፡14
8፥11 ዕብ4፥12

7፥44 *ለእግሬ ውሃ፤* ለእንግዳ ሊደረግለት የሚገባ አነስተኛ መስተንግዶ ነው::

7፥47 *እጅግ ወዳለች፤* ፍቅርዋ ይቅርታ ለማግኘቷ ማስረጃ ነው እንጂ፣ ከፍቅሯ የተነሣ ይቅርታ አላገኘችም:: በቍ 50 የተገለጸው ሐሳብም፣ ሴቲቱ በእምነት እንደ ዳነች በግልጽ ያመ ለክታል፤ ኤፌ 1፥7 ይመ::

7፥50 *እምነትሽ አድኖሻል፤* ኀጢአቷ ይቅር ስለ ተባለ፣ የእግ ዚአብሔርን ሰላም አግኝታለች (1፥79 እና የ 2፥4 ማብ ይመ)::

8፥1 *ኢየሱስ... አለፈ፤* ኢየሱስ የአገልግሎቱ ማእከል አድርጎ የነበረው ቅፍርናሆምን ሲሆን፣ ይሰብክ የነበረውም በምኵ ራብ ውስጥ ነበር፤ በገሊላ ባደረገው ሁለተኛው ጕዞም ከከተማ ወደ ከተማ እየተዘዋወረ ሰበከ፤ የመጀመሪያውን ጕዞ በተመለከተ 4፥43-44፤ ማቴ 4፥23-25፤ ማር 1፥38-39 ይመ:: ሦስተኛውንም ጕዞ በተመለከተ የ9፥1-6 ማብ ይመ:: *የእግዚአብሔርን መንግ ሥት፤* የ4፥43 ማብ ይመ::

8፥2 *መግደላዊት የተባለችው ማርያም፤* በመግደላ የምት ኖር ሴት ናት፤ እርሷም በም 7 ላይ የተጠቀሰችው ኀጢአተኛ ሴት ወይም የቢታንያዋ ማርያም አይደለችም (ዮሐ 11፥1)::

8፥3 *ሶስና፤* እዚህ ቦታ ከተጠቀሰው በስተቀር፣ ስለ እርሷ የሚታወቅ ነገር የለም:: *የሚያገለግሉት ነበሩ፤* ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱ፣ ለዕለት ኑሮአቸው የሚያስፈልጋቸውን ነገሮች ያገኙ የነበሩት በታምር ሳይሆን፣ የተዋለላቸውን ውለታ ባልዘነጉ እንደ ነዚህ ያሉ ሴቶች በሚያደርጉት ድጋፍ ነበር::

8፥4 *ምሳሌ፤* ከዚህ ጀምሮ ኢየሱስ ሰዎችን ለማስተማር ብዙ ምሳሌዎችን ተጠቅሞአል (የማቴ 13፥3፤ ማር 4፥2 ማብ ይመ):: ምሳሌዎቹ ከተለመዱ ሁኔታዎች ጋር የተዛመዱ በመሆ ናቸው፣ ውጤታማና በቀላሉ የሚታወሱ ነበሩ፤ እንዲሁም እነዚህ ምሳሌዎች የኢየሱስን ትምህርት የሚያብራሩ ቢሆኑም፣ ተጨማሪ ማብራሪያ የሚያስፈልጋቸው ምስጢር አዘል ትርጕሞችን ዐቅ ፈዋል:: እነዚህ ምስጢር አዘል ተምሳሌቶች በቅንነት ሰዎች በይበ ልጥ ለማወቅ ፍላጎት እንዲኖራቸው ያደርጉ ነበር (ቍ 10 ይመ):: የኢየሱስ ጠላቶችም፣ እርሱን ለመክሰስ የሚረዳቸውን ሐሳብ በቀ ጥታ ከእነዚህ ምሳሌዎች ማግኘት አልቻሉም:: የዘሪው ምሳሌ በተመሳሳይ ወንጌላት ውስጥ ተጽፈው ከሚገኙት ምሳሌዎች አንዱ ነው (ማቴ 13፥1-23፤ ማር 4፥1-20):: ሌሎቹም የሰናፍጭ ቅንጣትና (13፥19፤ ማቴ 13፥31-32፤ ማር 4፥30-32) የወይን ተክል ምሳሌዎች ናቸው (20፥9-19፤ ማቴ 21፥33-46፤ ማር 12፥1-12)::

8፥5 *ዘሩን ሊዘራ፤* በምሥራቅ አገሮች አንዳንድ ጊዜ፣ ዘር ከዘሩ በኋላ ማረስ የተለመደ ነበር:: በብዙ ማሳዎች ላይ አውራ መንገዶችና የእግር መንገዶች ያልፉ ስለ ነበር፣ በእነዚህ መን ገዶች ላይ ይጓዙ የነበሩ ሁሉ መሬቱን እንዲጠጥር በማድ ረጋቸው፣ የተዘራው ዘር ሥር መስደድ አይችልም ነበር::

8፥6 *ድንጋያማ ቦታ፤* በዐፈር የተሸፈነ ድንጋያማ መሬት ነው:: በእንዲህ ዐይነት መሬት ላይ የወረደ ዝናብ ወዲያውኑ ስለ ሚተን፣ መብቀል የጀመረው ዘር ጠውልጎ ይጠፋል (ማቴ 13፥5-6 ይመ)::

8፥8 *መቶ ዕጥፍ፤* የሉቃስ አቀራረብ ከማቴዎስና (13፥8) ከማርቆስ (4፥8) ጋር ሲነጻጸር በአጭሩ የቀረበ ቢሆንም፣ መሠ ረታዊ ሐሳቡ ግን አንድ ነው፤ ይኸውም፣ የምርት መጠን እያደገ መሄድ ከዐፈሩ ለምነት ጋር በቀጥታ የተያያዘ መሆኑን ነው:: *ይስማ፤* ስብከቱን የሚሰሙ ሰዎች ትምህርቱን አስተውለው ተግባ ራዊ እንዲያደርጉ የሚያሳስብ ጥሪ ነው::

8፥9 *ደቀ መዛሙርቱም፤* "ዐሥራ ሁለቱንና ሌሎችንም" ይጨምራል (ማር 4፥10)::

8፥10 *የእግዚአብሔርን መንግሥት ምስጢር፤* እግዚአብሔር በሚሰጠው መገለጥ ብቻ የሚታወቅ እውነት ነው (ከኤፌ 3፥2-5፤ 1ጴጥ 1፥10-12 ጋር ያነጻጽሩ):: የማር 4፥11 ይመ፣ *እያዩ ልብ እንዳይሉ፤* ከትንቢተ ኢሳይያስ የተወሰደው ይህ ጥቅስ (6፥9)፣ አንዳንዶች እንዳያስተውሉ የተወሰኑ መሆናቸውን የሚያሳይ ሳይ ሆን፣ የኢየሱስን መልእክት ለመቀበል ፈቃደኛ ካልሆኑ ሰዎች፣ እውነት የተደበቀች መሆኗን የሚያመለክት ነው:: የመጨረሻ ዕጣ ፈንታቸው ምን እንደሚሆን በማቴ 13፥14-15 ተገልጾአል (የማር 4፥12 ማብ ይመ)::

8፥11 *የእግዚአብሔር ቃል፤* ከእግዚአብሔር የሚመጣውን መልእክት ማለት ነው::

8፥12 *አምነው እንዳይድኑ፤* የዲያብሎስ ዐላማ፣ ሰዎች

ቃሉን ከልባቸው የሚወስድባቸው ናቸው። [13]በድንጋያማ ቦታ ላይ የወደቀውም ቃሉን ሲሰሙ በደስታ የሚቀበሉ ናቸው፤ እነዚህ ለጊዜው ያምናሉ እንጂ ሥር ስለሌላቸው በፈተና ጊዜ ፈጥነው የሚክዱ ናቸው። [14]በእሾኽ መካከል የወደቀውም ቃሉን የሚ ሰሙት ናቸው፤ እነዚህም ውለው አድረው በምድራዊ ሕይወት ጭንቀት፣ በባለጠግነትና ተድላ ደስታ ታንቀው በሚገባ አያፈሩም። [15]በመልካም መሬት ላይ የወደቀውም ቃሉን ቅንና በጎ በሆነ ልብ ሰምተው የሚጠብቁ፣ ታግሠውም በመጽናት ፍሬ የሚያፈሩ ናቸው።

### በመቅረዝ ላይ ያለ መብራት

[16]"መብራትን አብርቶ ጋን ውስጥ ወይም በዐልጋ ሥር የሚያስቀምጥ ማንም የለም፤ ይልቁንም ወደ ቤት የሚገቡ ብርሃኑን እን ዲያዩ በመቅረዝ ላይ ያስቀምጠዋል። [17]የማ ይገለጥ የተሰወረ፣ የማይታወቅ ወደ ብርሃን የማይወጣ፣ የተደበቀ ነገር የለምና። [18]እንግ ዲህ እንዴት እንደምትሰሙ ተጠንቀቁ፤ ላለው ይጨመርለታልና፤ ከሌለው ሁሉ ግን ያው ያለው የሚመስለው እንኳ ይወሰድበ ታል።"

### የኢየሱስ እናትና ወንድሞች

8፥19-21 ተጓ ምብ – ማቴ 12፥46-50፤ ማር 3፥31-35

[19]ከዚህ በኋላ የኢየሱስ እናትና ወንድሞቹ እርሱ ወዳለበት መጡ፤ እነርሱም ከሕዝቡ ብዛት የተነሣ ወደ እርሱ ሊቀርቡ አልቻ ሉም። [20]በዚህ ጊዜ፣ "እናትህና ወንድሞችህ ሊያዩህ ፈልገው በውጭ ቆመዋል" የሚል ወሬ ደረሰው።

[21]እርሱም መልሶ፣ "እናቴና ወንድሞቼስ የእግዚአብሔርን ቃል ሰምተው የሚያደርጉት ናቸው" አላቸው።

8፥13 ማቴ11፥6
8፥14 ማቴ19፥23፤1 ጢሞ6፥9፡10፡17
8፥16 ማቴ5፥15
8፥17 ማቴ10፥26፤ ማር4፥22፤ሉቃ12፥2
8፥18 ማቴ25፥29
8፥20 ዮሐ7፥5
8፥21 ሉቃ6፥47፤ 11፥28፤ዮሐ14፥21
8፥24 መዝ107፥ 29፤ሉቃ4፥35፤ 5፥5፤ሉቃ39፥41፤ ዮሐ1፥15
8፥28 ማቴ8፥29፤ ማር5፥7

### ኢየሱስ ማዕበሉን ጸጥ አደረገ

8፥22-25 ተጓ ምብ – ማቴ 8፥23-27፤ ማር 4፥36-41
8፥22-25 ግመ – ማር 6፥47-52፤ ዮሐ 6፥16-21

[22]ከዕለታት አንድ ቀን ኢየሱስ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ጀልባ ላይ ወጣ፤ ኢየሱ ስም፤ "ወደ ባሕሩ ማዶ እንሻገር" አላቸው፤ ከዚያም ጕዞ ቀጠሉ። [23]እየተጓዙ ሳሉም ኢየ ሱስ እንቅልፍ ወስዶት ተኛ፤ በዚህ ጊዜ በባ ሕሩ ላይ ማዕበል ተነሣ፤ ውሃውም ጀልባዋን ዘልቆ ስለ ገባ፣ አደጋ አፋፍ ላይ ደረሱ።

[24]ደቀ መዛሙርቱም ቀርበው፣ "ጌታ ሆይ፤ ጌታ ሆይ፤ ማለቃችን እኮ ነው!" እያሉ ቀሰቀ ሱት።

እርሱም ነቅቶ ነፋሱንና፣ የውሃውን መና ወጥ ገሠጸ፤ በዚህ ጊዜ ነፋሱም፣ ነውጡም ተወ፤ ጸጥታም ሆነ። [25]እርሱም ደቀ መዛ ሙርቱን፣ "እምነታችሁ የት አለ?" አላቸው።

እነርሱም በፍርሀትና በመደነቅ፣ "ይህ ነፋስ ንና ውሃን የሚያዝ፣ እነርሱም የሚታዘዙለት ለመሆኑ እርሱ ማን ነው?" ተባባሉ።

### አጋንንት ያደረበት ሰው መፈወሱ

8፥26-37 ተጓ ምብ – ማቴ 8፥28-34
8፥26-39 ተጓ ምብ – ማር 5፥1-20

[26]ከዚህ በኋላ ከገሊላ ባሻገር ወዳለው ወደ ጌርጌሴኖን[a] አገር በጀልባ ተሻገሩ። [27]ኢየ ሱስ ከጀልባዋ ወደ ምድር በወረደ ጊዜ፣ አጋንንት ያደረበት አንድ ሰው ከከተማ ወጥቶ አገኘው፤ ይህ ሰው ለብዙ ጊዜ ልብስ ሳይለብስ፣ በቤትም ሳይኖር የመቃብርን ስፍራ ቤቱ ያደረገ ነበር። [28]ኢየሱስንም ባየው ጊዜ እየጮኸ ፊቱ ተደፋ፤ በታላቅ ድምፅም፣ "የልዑል እግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ሆይ፤ ከእኔ ጋር ምን ጕዳይ አለህ? እንዳታሠቃየኝ እለ ምንሃለሁ" አለ። [29]ርኩሱ[b] መንፈስ ይህን ያለው ከሰውየው እንዲወጣ ኢየሱስ አዞት ስለ ነበር ነው።

[a]26 አንዳንድ ቅጆች ጋድሬኔስ፣ ሌሎች ቅጆች ደግሞ ጌርጌ ሴኔስ ይላሉ፤ ቍ 37 ይመ
[b]29 ወይም ክፉ

የእግዚአብሔርን ቃል በማስተዋል እንዳይሰሙ ማድረግ፣ በሕ ይወታቸውም ተግባራዊ እንዳያደርጉና እንዳይድኑ ነው።

8፥13 *ለጊዜው ያምናሉ፤* እንደዚህ ያለው እምነት የይስሙላ በመሆኑ ድነት አያስገኝም፤ *ያዕቆብም* "የሞተ" (ያዕ 2፥17፡26) ወይም "ከንቱ" ነው ብሎታል (ያዕ 2፥20)። *በመቅረዝ ላይ ያስቀ ምጠዋል፤* የማቴ 5፥15 ማብ ይመ።

8፥16 *መብራትን አብርቶ፤* ምንም እንኳን ኢየሱስ አብዛ ኛው ሐሳቡን በምሳሌዎች ውስጥ የገለጸ ቢሆንም፣ ደቀ መዛሙርቱ እውነቶችን በተቻለ መጠን እንዲያሳውቁ ዕቅዱ ነበር (የ11፥33 ማብ ይመ)። *በመቅረዝ ላይ ያስቀምጠዋል፤* የማቴ 5፥15 ማብ ይመ።

8፥17፤ በቍጥር 16 ላይ ያለውን ሐሳብ የሚያብራራ ነው (ከ12፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። ደቀ መዛሙርቱም፣ ለሁሉ ሊዳረስ የሚ ገባውን ወንጌል መልእክት ለማብሰር ተዘጋጅተዋል።

8፥18 *እንዴት እንደምትሰሙ ተጠንቀቁ፤* ደቀ መዛሙርቱ የሰሙት ለራሳቸው ብቻ ሳይሆን፣ ለሚያገለግሉትም ሕዝብ ጭምር ነው (ማር 4፥24 ይመ፤ ያዕ 1፥19-22 ጋር ያነጻጽሩ)። በተግባር ያላዋሉት እውነት ይጠፋል (19፥26)፣ በተግባር የተገለጸ እውነት ግን ይበዛል።

8፥19 *የኢየሱስ እናትና ወንድሞቹ... መጡ፤* የማር 3፥21 ማብ ይመ። ወደ ኢየሱስ የመጡበት ዐላማ በማር 3፥21፡ 31-32 ላይ ተገልጾአል፤ ይኸውም "አብዶአል" በማለት ካለበት አስቸጋሪ ሁኔታ ነጻ እንዲሆን ፈልገው ሳይሆን አይቀርም። *ወንድሞቹ፤* ይህን በተመለከተ፣ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን የነበሩ ምሁራን ልዩ ልዩ ትርጓሜዎችን ሰጥተዋል፤ ለምሳሌ፣ ዮሴፍ ቀድሞ ከነበረው ጋብቻ የወለዳቸው ናቸው (ኤጲፋንዮስ)፣ የአያቶቹ ወይም የአክስ ቶቹ ልጆች ናቸው (ዮሮም)፣ እንዲሁም ከዮሴፍና ከማርያም የተወለዱ፣ የኢየሱስ ታናሽ ወንድሞች ናቸው (ሔልቪዲየስ)። የአራት ወንድሞቹና የእህቶቹ ስም በማር 6፥3 ላይ ተገልጾአል፤ የዮሴፍ ስም በዚህ ቍጥር ላይ አለመገለጹ፣ ምናልባት ከዚህ ሁኔታ በፊት ስለ ሞተ ሊሆን ይችላል።

*8፥21፤* ኢየሱስ እንዲህ ያለ መልስ መስጠቱ፣ ከሥጋ ዘመዶቹ ጋር ያለውን ግንኙነት ላለመቀበል ፈልጎ ሳይሆን፣ በእርሱ ካመኑት ጋር ያለው መንፈሳዊ ግንኙነት የላቀ መሆኑን በአጽንዖት ለማሳየት ነው።

8፥23 *ማዕበል፤* የማር 4፥37 ማብ ይመ።

8፥26 *ጌርጌሴኖን አገር፤* የማቴ 8፥28፤ ማር 5፥1 ማብ ይመ።

8፥27 *አጋንንት ያደረበት... ሰው፤* የ4፥33 ማብ ይመ። በማቴዎስ ወንጌል የተጠቀሰው "አጋንንት ያደሩባቸው ሁለት ሰዎች" ሲሆን (8፥28)፣ በማርቆስና (5፥2) ሉቃስ ግን፣ "አንድ ሰው" ነው። *የመቃብር፤* ሰዎች የማይፈልጉት ገለልተኛ ስፍራ ነው። (የማር 5፥3 ማብ ይመ)።

8፥28 *የልዑል እግዚአብሔር ልጅ፤* ከ1፥32፤ 4፥34 ጋር ያነጻጽሩ፤ "የልዑል እግዚአብሔር" የሚለውን መጠሪያ አዘውትረው የሚጠቀሙት አሕዛብ ነበሩ (ዘፍ 14፥19 እና ማብ ይመ፤ ሐዋ 16፥17 ይመ)፤ እዚህ ላይ መጠቀሱም፣ ሰውየው አይሁዳዊ አለ መሆኑን የሚያመለክት ነው (የማር 1፥24 ማብ ይመ)።

ርኩሱ መንፈስ በየጊዜው ስለሚነዳበት ሰውየው በሰንሰለትና በእግር ብረት እየታሰረ ቢጠበቅም የታሰረበትን ሰንሰለት እየበጣጠሰ ያደረበት ጋኔን ወደ በረሓ ይነዳው ነበር::

[30]ኢየሱስም፣ "ስምህ ማን ነው?" ብሎ ጠየቀው::

እርሱም ብዙ አጋንንት ገብተውበት ስለ ነበር፣ "ሌጌዎን" አለው:: [31]አጋንንቱም እንጦርጦስ ግቡ ብሎ እንዳያዛቸውም አጥብቀው ለመኑት::

[32]በዚያም አካባቢ በተራራ ወገብ ላይ የብዙ ዐሣማ መንጋ ተሰማርቶ ነበር፤ አጋንንቱም ወደ ዐሣማው መንጋ ግቡ ብሎ እንዲፈቅድላቸው ለመኑት፤ እርሱም ፈቀደላቸው:: [33]አጋንንቱም ከሰውየው ወጥተው ወደ ዐሣማዎቹ ገቡ፤ የዐሣማውም መንጋ በገደሉ አፋፍ ቍልቍል በመንደርደር ባሕሩ ውስጥ ገብቶ ሰጠመ::

[34]እረኞቹም የሆነውን ነገር ባዩ ጊዜ፣ ሸሽተው በመሄድ በከተማውና በገጠሩ አወሩ:: [35]ሕዝቡም የተደረገውን ነገር ለማየት ከያሉበት ወጥተው ወደ ኢየሱስ መጡ:: አጋንንት የወጡለትም ሰው ልብስ ለብሶ፣ ወደ ልቦናው ተመልሶ፣ በኢየሱስም እግር ሥር ተቀምጦ ባዩት ጊዜ ፈሩ:: [36]በአጋንንት የተያዘው ሰው ሲድን ያዩትም፣ እንዴት እንደ ዳነ ለሕዝቡ አወሩላቸው:: [37]የጌርጌሴኖን አካባቢ ሰዎችም ሁሉ ታላቅ ፍርሀት ስላደረባቸው፣ ከዚያ እንዲሄድላቸው ኢየሱስን ለመኑት፤ እርሱም ወደ ጀልባው ገብቶ ተመልሶ ሄደ::

[38]አጋንንት የወጡለትም ሰው አብሮት ለመሆን ኢየሱስን ለመነው፤ እርሱ ግን እንዲህ ሲል አሰናበተው፤ [39]"ወደ ቤትህ ተመልሰህ፣ እግዚአብሔር ያደረገልህን ታላቅ ነገር ተናገር::" ሰውየውም ኢየሱስ ያደረገለትን ታላቅ ነገር በከተማው ሁሉ በይፋ እየተናገረ ሄደ::

## የሞተችው ልጅና የታመመችው ሴት

8፥40-56 ተጓ ምብ – ማቴ 9፥18-26፤ ማር 5፥22-43

[40]ሕዝቡ ሁሉ መምጣቱን ይጠባበቁ ስለ ነበር፣ ኢየሱስ በተመለሰ ጊዜ በደስታ ተቀበሉት:: [41]በዚህ ጊዜ ኢያኢሮስ የተባለ የምኵራብ አለቃ መጥቶ፣ በኢየሱስ እግር ላይ በመውደቅ ወደ ቤቱ እንዲሄድለት ለመነው፤ [42]ይህን ልመና ያቀረበው ዕድሜዋ ዐሥራ ሁለት ዓመት የሆነ አንዲት ልጅ ስለነበረችው ነው፤ እርሷ በሞት አፋፍ ላይ ነበረች:: ወደዚያው እያመራ ሳለ፣ ሕዝቡ በመጋፋት እጅግ ያጨናንቀው ነበር:: [43]ዐሥራ ሁለት ዓመት ደም ሲፈሳት የኖረች አንዲት ሴት ነበረች፤ ያላትን ሁሉ ለባለ መድኀኒቶች ጨርሳ[†] ሊፈውሳትም የቻለ ማንም አልነበረም:: [44]እርሷም ከበስተ ኋላው ተጠግታ የልብሱን ጫፍ ነካች፤ ይፈስ የነበረው ደሟም ወዲያው ቆመ::

[45]ኢየሱስም፣ "የነካኝ ማነው?" አለ::

ሁሉም መንካታቸውን በካዱ ጊዜ ጴጥሮስ፣ "ጌታ ሆይ፤ ሕዝቡ ሁሉ ከቦህ በግፊያ እያስጨነቀህ ነው" አለው::

[46]ኢየሱስ ግን፣ "አንድ ሰው ነክቶኛል፤ ኀይል ከእኔ እንደ ወጣ ዐውቃለሁና" አለ::

[47]ሴትዮዋም ሳትታወቅ መሄድ እንዳልቻለች በተረዳች ጊዜ፣ እየተንቀጠቀጠች መጥታ በፊቱ ተደፋች፤ ለምን እንደ ነካችውና እንዴት ወዲያው እንደ ተፈወሰች በሕዝቡ ሁሉ ፊት ተናገረች:: [48]እርሱም፣ "ልጄ ሆይ፤ እምነትሽ ፈውሶሻል፤ በሰላም ሂጂ" አላት::

[49]ኢየሱስ ገና እየተናገረ ሳለ፣ አንድ ሰው ከምኵራብ አለቃው ከኢያኢሮስ ቤት መጥቶ፣ "ልጅህ ሞታለች፤ ከዚህ በኋላ መምህሩን አታድክመው" አለው::

[50]ኢየሱስም ይህን ሰምቶ ኢያኢሮስን፣ "አይዞህ አትፍራ፤ እመን ብቻ፤ ልጅህ ትድናለች" አለው::

[51]ወደ ኢያኢሮስ ቤት ሲገባም ከጴጥሮስ፣ ከዮሐንስና ከያዕቆብ እንዲሁም ከልጅቱ አባትና እናት በቀር ማንንም አብሮት እንዲገባ አልፈቀደም:: [52]በዚህ ጊዜ ሰዎቹ ሁሉ እያለቀሱላት ዋይ ዋይ ይሉ ነበር:: እርሱ ግን፣ "አታልቅሱ፤ ተኝታለች እንጂ አልሞተችም" አላቸው::

[†]43 አያሌ ቅጆች *ያላትን ሁሉ ለባለ መድኀኒቶች ጨርሳ* የሚለው የላቸውም

8፥31 ራእ9፥1፤ 2፡11፤ 11፥7፤ 17፥8፤20፥1፡3
8፥33 ቍ22፡23
8፥35 ሉቃ10፥39
8፥36 ማቴ4፥24
8፥37 ሐሥ16፥39
8፥41 ቍ49፤ ማር5፥22
8፥43 ዘሌ15፥25-30
8፥44 ማቴ9፥20
8፥45 ሉቃ5፥5
8፥46 ማቴ14፥36፤ ማር3፥10፤ሉቃ5፥17፤ 6፥19
8፥48 ማቴ9፥22፤ ሐሥ15፥33
8፥49 ቍ41
8፥51 ማቴ4፥21
8፥52 ማቴ9፥24፤ ሉቃ23፥27

8፥30 *ስምህ ማን ነው?* ኢየሱስ የጠየቀውን ሰውየውን ሲሆን፣ መልስ የሰጡት ግን፣ አጋንንቱ ናቸው፤ ይህ የሚያሳየው ሰውየው በእነርሱ ቍጥጥር ሥር መሆኑን ነው:: *ሌጌዎን* የማር 5፥9 ማብ ይመ::

8፥31 *እንጦርጦስ፤* ሰይጣንና ክፉ መናፍስት ታስረው የሚቈዩበት ስፍራ ነው (የራእ 9፥1 ማብ ይመ)::

8፥32 *ዐሣማው፤* በአይሁዳውያን ዘንድ፣ ዐሣማ እንደ ርኩስ ስለሚቈጠር፣ ሥጋውን መብላት የተከለከለ ነበር (ዘሌ 11፥7-8)፤ ይሁን እንጂ በዴካፖሊስ ከተማ በብዛት የሚኖሩት አሕዛብ ናቸው:: *እርሱም ፈቀደላቸው፤* የማቴ 8፥32 ማብ ይመ::

8፥39 *ወደ ቤትህ ተመልሰህ፣ እግዚአብሔር ያደረገልህን ታላቅ ነገር ተናገር፤* ሰውየው ኢየሱስን ለመከተል ቢፈልግም፣ በተወለደበት አገር የተደረገለትን ታምር እንዲመሰክር ታዘዘ:: በዚህ ቦታ የኢየሱስን አገልግሎት የሚያደናቅፍ አደገኛ ሁኔታ አልነበረም (የማር 5፥19 ማብ ይመ)::

8፥41 *የምኵራብ አለቃ፤* የአምልኮ ሥርዐትን መፈጸም፣ አገልጋዮችን መምረጥና ሥርዐት እንዲጠበቅ ማድረግ የእርሱ ኀላፊነት ነበር (የማር 5፥22 ማብ ይመ)::

8፥43 *ደም ሲፈሳት፤* ለዐሥራ ሁለት ዓመታት ይፈሳት በነበረ ደም ምክንያት፣ በሥርዐቱ መሠረት ርኩስ ሆና ተቈጥራ ነበር (ዘሌ 15፥19-30 ይመ):: *ሊፈውሳትም የቻለ ማንም አልነበረም፤* ይህ ሁኔታ ከማር 5፥26 ጋር ሲነጻጸር፣ ሐኪሞች ያድናት ዘንድ አለመቻላቸውን የሕክምና ባለሙያው ሉቃስ፣ መግለጽ አለመፈለጉን በግልጽ ያመለክታል::

8፥45 *የነካኝ ማነው?* ሴትየዋ በኅብረተሰቡ ዘንድ ተቀባይነት እንድታገኝና ተሰብስቦ ለነበረውም ሕዝብ ምስክር እንዲሆን፣ ኢየሱስ ይህን ጥያቄ በመጠየቅ የተደረገውን ታምር ይፋ አደረገ::

8፥46 *ኀይል ከእኔ እንደ ወጣ፤* የማር 5፥30 ማብ ይመ::

8፥48 *ልጄ ሆይ፤* ርኅራኄ የተሞላ አጠራር ነው (ከ 23፥28 ጋር ያነጻጽሩ):: *በሰላም ሂጂ፤* ከ7፥50 ጋር ያነጻጽሩ::

8፥50 *ትድናለች፤* የማር 5፥34 ማብ ይመ::

8፥52 *እያለቀሱላት ዋይ ዋይ ይሉ፤* የማር 5፥38 ማብ ይመ:: *ተኝታለች እንጂ አልሞተችም፤* እንደ ሞተች አትቀ

⁵³ሰዎቹም መሞቷን ስላወቁ ሣቁበት። ⁵⁴እርሱ ግን እጇን ይዞ፣ "ልጂ ሆይ፤ ተነሺ" አላት። ⁵⁵የልጅቷም መንፈስ ተመለሰ፤ ወዲያውም ተነሥታ ቆመች፤ ኢየሱስም የሚበላ ነገር እንዲሰጧት አዘዛቸው። ⁵⁶ወላጆቿም ተደነቁ፤ እርሱ ግን የሆነውን ነገር ለማንም እንዳያወሩ አዘዛቸው።

## የዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት መላክ

9፥3-5 ተጓ ምብ – ማቴ 10፥9-15፤ ማር 6፥8-11
9፥7-9 ተጓ ምብ – ማቴ 14፥1፡2፤ ማር 6፥14-16

**9** ኢየሱስም ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት በአንድነት ጠርቶ አጋንንትን ሁሉ እንዲያወጡ፣ ደዌንም እንዲፈውሱ ኀይልና ሥልጣን ሰጣቸው፤ ²ደግሞም የእግዚአብሔርን መንግሥት እንዲሰብኩና የታመሙትን እንዲፈውሱ ላካቸው፤ ³እንዲህም አላቸው፤ "ለመንገዳችሁ በትር ቢሆን፣ ከረጢትም ቢሆን፣ እንጀራም ቢሆን፣ ገንዘብም ቢሆን፣ ሁለት ሁለት እጀ ጠባብም መያዝ አያስፈልጋችሁም። ⁴ከዚያ ከተማ እስክምትወጡ ድረስ መጀመሪያ በገባችሁበት በማንኛውም ቤት ቈዩ። ⁵የከተማው ሰዎች ሳይቀበሏችሁ ቀርተው ከተማቸውን ለቃችሁ ስትሄዱ፣ ምስክር እንዲሆንባቸው የእግራችሁን ትቢያ አራግፉችሁ ውጡ።" ⁶እነርሱም በዚሁ መሠረት ወጥተው ወንጌልን እየሰበኩ በየቦታው ሁሉ ሕመምተኞችን እየፈወሱ በየመንደሩ ያልፉ ነበር።

⁷የአራተኛው ክፍል ገዥ ሄሮድስም፣ በዚህ ጊዜ የሆነውን ነገር ሁሉ ሰምቶ በሁኔታው ተደናገረ፤ ምክንያቱም አንዳንድ ሰዎች ዮሐንስ ከሙታን እንደ ተነሣ ያወሩ ነበር፤ ⁸ሌሎች ኤልያስ እንደ ተገለጠ፣ ሌሎች ደግሞ ከቀድሞዎቹ ነቢያት አንዱ ከሙታን እንደ ተነሣ ይናገሩ ነበር። ⁹ሄሮድስም፣ "መጥምቁ ዮሐንስን እኔው ራሴ ዐንገቱን ቈርጬው ሞቶአል፤ ታዲያ፣ ስለ እርሱ እንዲህ ሲወራ የምሰማው ይህ ሰው ማነው?" አለ፤ በዐይኑም ሊያየው ይሻ ነበር።

## ኢየሱስ አምስት ሺህ ሰዎችን መገበ

9፥10-17 ተጓ ምብ - ማቴ14፥13-21፤ ማር 6፥32-44፤ ዮሐ 6፥5-13
9፥13-17 ማመ - 2ነገ 4፥42-44

¹⁰ሐዋርያትም ተመልሰው በመጡ ጊዜ ያደረጉትን ሁሉ ነገሩት፤ እርሱም ይዞአቸው ቤተ ሳይዳ ወደምትባል ከተማ በመሄድ ለብቻው ገለል አለ። ¹¹ሕዝቡም ይህን ዐውቀው ተከተሉት፤ እርሱም ተቀብሎአቸው ስለ እግዚአብሔር መንግሥት ይነግራቸው ነበር፤ ፈውስ የሚያስፈልጋቸውንም ፈወሳቸው።

¹²ቀኑም ሊመሽ ሲል፣ ዐሥራ ሁለቱ ወደ እርሱ ቀርበው፣ "ያለነው በምድረ በዳ ስለ ሆነ፣ ሕዝቡ ወደ አካባቢው መንደርና ገጠር ሄደው ማደሪያና ምግብ እንዲፈልጉ አሰናብታቸው" አሉት።

¹³እርሱ ግን፣ "የሚበሉትን እናንተው ስጧቸው" አላቸው።

እነርሱም፣ "ለዚህ ሁሉ ሕዝብ የሚበቃ ምግብ ሄደን ካልገዛን በስተቀር፣ እኛ ያለን ከአምስት እንጀራና ከሁለት ዓሣ አይበልጥም" አሉት፤ ¹⁴አምስት ሺህ ያህል ወንዶች በዚያ ነበሩና።

ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱን፣ "ሕዝቡን በአምሳ በአምሳ ሰው መድባችሁ አስቀምጧቸው" አላቸው። ¹⁵ደቀ መዛሙርቱም በታዘዙት መሠረት ሰዎቹ እንዲቀመጡ አደረጉ። ¹⁶እርሱም አምስቱን እንጀራና ሁለቱን ዓሣ ይዞ ወደ ሰማይ አሻቅቦ እያየ ባረካቸው፤ ቈርሶም ለሕዝቡ እንዲያቀርቡ ለደቀ መዛሙርቱ ሰጠ። ¹⁷ሁሉም በልተው ጠገቡ፤

8፥54 ሉቃ7፥14
8፥56 ማቴ8፥4
9፥1 ማቴ4፥23፤ 10፥1፤ሉቃ5፥17
9፥2 ማቴ3፥2
9፥3 ሉቃ10፥4፤ 22፥35
9፥5 ማቴ10፥14
9፥7 ማቴ3፥1፤14፥1
9፥8 ቍ19፤ማቴ 11፥14፤ዮሐ1፥21
9፥9 ሉቃ23፥8
9፥10 ማቴ11፥21፤ ማር6፥30
9፥11 ቍ2፤ ማቴ3፥2
9፥16 ማቴ14፥19

ርም ማለቱ ነው (በዮሐ 11፥11-14 ስለ አልዓዛር የተጻፈውን ተመሳሳይ አገላለጽ ይመ)።

8፥56 *እንዳያወሩ አዘዛቸው፤* የማቴ 8፥4፤ ማር 5፥43 ማብ ይመ። ኢየሱስ ከሞት እንደሚያስነሣ በዚህ ጊዜ ቢታወቅ አገልግሎቱ ላይ ዕንቅፋት ይፈጠር ነበር።

*9፥1-6፤* ኢየሱስ፣ እንደሰበከውና እንዳስተማረው ዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት እንዲሁ ያደርጉ ዘንድ በላካቸው ጊዜ፣ ለአገልግሎቱ አዲስ ምዕራፍ ከፈተ (ማቴ 9፥35)። ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱ ወደ ገሊላ ሲሄዱ፣ ይህ ሦስተኛ ጊዜያቸው ነበር (የ8፥1 ማብ ይመ)። በመጀመሪያው ጕዞ ኢየሱስ ወደ ገሊላ የሄደው ከአራቱ ዓሣ አጥማጆች ጋር ነበር፤ በሁለተኛው ጕዞ ዐሥራ ሁለቱም ሐዋርያት ከእርሱ ጋር ሄደው ነበር፤ በሦስተኛው ጕዞ ግን፣ ኢየሱስ ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት ጥንድ ጥንድ አድርጎ ከላካቸው በኋላ ለብቻቸው ሄዱ።

9፥1 *ዐሥራ ሁለቱን፤* ሐዋርያት ናቸው (6፥13 ይመ)። *ኀይልና ሥልጣን፤* የፈውስ ልዩ ኀይል (5፥17፤ 8፥46 ይመ)፣ እንዲሁም የማስተማርና ክፉ መናፍስትን የመቃወም ሥልጣን ነው። *አጋንንት፤* ክፉ መናፍስት ማለት ነው (የ4፥33 ማብ ይመ)።

9፥3 *መያዝ አያስፈልጋችሁም፤* ጕዞአቸውን የሚያሰናክል ሸክምና የዕለት ምግብም እንኳ ቢሆን መያዝ የለባቸውም፤ በየዕለቱ የሚያስፈልጋቸውን ነገር ከሚያስተናግዱአቸው ሰዎች ማግኘት ነበረባቸው (የማር 6፥8 ማብ ይመ)።

9፥4 *በገባችሁበት... ቈዩ፤* በአንድ ማኅበረ ሰብ መካከል ወንጌል ለመስበክ ሲገዙ የተሻለ ማረፊያ በመፈለግ ከአንዱ ቤት ወደ ሌላው መዘዋወር የለባቸውም፤ ነገር ግን በመጀመሪያ ያረፉበት ቤት፣ የአገልግሎታቸው ማእከል መሆን አለበት።

9፥5 *የእግራችሁን ትቢያ አራግፉችሁ፤* የእግዚአብሔርን ቃል ባለማቀበላቸው፣ ዕዳው በእነርሱ ላይ መሆኑን ለማግለጽ፣ እንዲሁም ከእነርሱና የእነርሱ ከሆነው ነገር ጋር ምንም ግንኙነት ከእንግዲህ ወዲያ እንደማያደርጉ ለማሳየት የሚጠቀሙበት ምልክት ነው (10፥11 ይመ፤ የማቴ 10፥14፤ የሐሥ 13፥51 ማብ ይመ)።

9፥7 *የአራተኛው ክፍል ገዥ ሄሮድስ፤* የማቴ 14፥1 ማብ ይመ። *ዮሐንስ ከሙታን እንደ ተነሣ፤* የማር 6፥16 ማብ ይመ። ሉቃስ ስለ ዮሐንስ ሞት ቢጽፍም (ቍ 9)፣ ስለ አሟሟቱ ግን ምንም አልተጠቀሰም (ማቴ 14፥1-12፤ ማር 6፥17-29)።

9፥8 *ኤልያስ እንደ ተገለጠ፤* የ1፥17፤ ማር 9፥12 ማብ ይመ።

9፥9 *ሊያየውም ይሻ ነበር፤* ጌታ ኢየሱስ ተከሶ እስከ ቀረበበት ጊዜ ድረስ፣ ሄሮድስ እርሱን ለማየት የነበረው ፍላጎት አልተሳካም ነበር (23፥8-12)።

*9፥10-17፤* ከኢየሱስ ትንሣኤ በተጨማሪ በአራቱም ወንጌሎች ተጠቅሶ የሚገኘው ታምር፣ ኢየሱስ አምስት ሺህ ሰዎችን መመገቡ ነው (የማር 6፥30-44፤ ዮሐ 6፥1-14 ማብ ይመ)።

9፥10 *ቤተ ሳይዳ፤* የማቴ 11፥21 ማብ ይመ። ኢየሱስ፣ ከዚህ ከተማ ወጣ ወዳለ ስፍራ ለዕረፍት ሳይሄድ አይቀርም (ቍ 12)።

9፥12 *ቀኑም ሊመሽ ሲል፤* ኢየሱስ ከሰበከና በሽተኞችን ከፈወሰ በኋላ፣ ደቀ መዛሙርቱ ስለ ምግብና ማደሪያ ጥያቄ አቀረቡ፣ በዮሐ 6፥5 ላይ ጥያቄውን ያቀረበው ኢየሱስ ቢሆንም፣ በተመሳሳይ ወንጌላት ውስጥ ግን፣ ጥያቄውን ያቀረቡት ደቀ መዛሙርቱ ናቸው።

9፥14 *በአምሳ በአምሳ ሰው መድባችሁ አስቀምጧቸው፤* የማር 6፥40 ማብ ይመ።

ደቀ መዛሙርቱም ከእነርሱ የተረፈውን ቍርስራሽ እንጀራ ዐሥራ ሁለት መሶብ አነሡ።

## ጴጥሮስ ስለ ኢየሱስ ማንነት መሰከረ

9፥18-20 ተጓ ምብ – ማቴ 16፥13-16፤ ማር 8፥27-29
9፥22-27 ተጓ ምብ - ማቴ 16፥21-28፤ ማር 8፥31-9፥1

[18]ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ብቻውን ይጸልይ ነበር፤ ደቀ መዛሙርቱም ከእርሱ ጋር ነበሩ፤ እርሱም፣ “ሕዝቡ እኔን ማን ነው ይሉኛል? ” ብሎ ጠየቃቸው።

[19]እነርሱም፣ “አንዳንዶች መጥምቁ ዮሐንስ፣ ሌሎች ኤልያስ፣ ሌሎች ደግሞ ከቀድሞ ነቢያት አንዱ ከሙታን ተነሥቶአል ይላሉ” አሉት።

[20]እርሱም፣ “እናንተስ ማን ነው ትሉኛላችሁ?” አላቸው።

ጴጥሮስም፣ “አንተ የእግዚአብሔር መሲሕ[a] ነህ” ሲል መለሰለት።

[21]ኢየሱስም ይህን ለማንም እንዳይናገሩ አጥብቆ አስጠነቀቃቸው፤ [22]ደግሞም፣ “የሰው ልጅ ብዙ መከራ መቀበል ይገባዋል፤ እንዲሁም በሽማግሌዎች፣ በካህናት አለቆችና በጸሐፍት ዘንድ መናቅ፣ መገደልና በሦስተኛው ም ቀን ከሙታን መነሣት አለበት” አላቸው።

[23]ከዚያም ለሁሉም እንዲህ አላቸው፤ “በኋላዬ ሊመጣ የሚፈልግ ማንም ቢኖር ራሱን ይካድ፤ መስቀሉንም በየዕለቱ ተሸክሞ ይከተለኝ፤ [24]ምክንያቱም ነፍሱን ሊያድናት የሚፈልግ ሁሉ ያጠፋታል፤ ነፍሱን ስለ እኔ ብሎ የሚያጠፋት ግን ያድናታል። [25]ሰው ዓለምን ሁሉ ቢያተርፍ ነፍሱን ግን ቢያጠፋ ወይም ቢያጐድል ጥቅሙ ምንድን ነው? [26]ማንም በእኔና በቃሌ ቢያፍር፣ የሰው ልጅ በራሱ ክብር እንዲሁም በአብና በቅዱሳን መላእክት ክብር ሲመጣ ያፍርበታል። [27]እውነት እላችኋለሁ፤ እዚህ ከቆሙት መካከል የእግዚአብሔርን መንግሥት ሳያዩ ሞትን የማይቀምሱ ሰዎች አሉ።”

## የኢየሱስ መልክ መለወጥ

9፥28-36 ተጓ ምብ – ማቴ 17፥1-8፤ ማር 9፥2-8

[28]ኢየሱስ ይህን ከተናገረ ከስምንት ቀን ያህል በኋላ ጴጥሮስን፣ ዮሐንስንና ያዕቆብን ይዞ ሊጸልይ ወደ አንድ ተራራ ወጣ። [29]በመጸለይ ላይ እንዳለም የፊቱ መልክ ተለወጠ፤ ልብሱም እንደ መብረቅ የሚያንጸባርቅ ነጭ ሆነ። [30]እነሆ፤ ሁለት ሰዎች፣ እነርሱም ሙሴና ኤልያስ ከእርሱ ጋር ይነጋገሩ ነበር፤ [31]በክብርም ተገልጠው፣ በኢየሩሳሌም ይፈጸም ዘንድ ስላለው ከዚህ ዓለም ስለ መለየቱ ይናገሩ ነበር። [32]ጴጥሮስና አብረውት የነበሩት ግን እንቅልፍ ተጭኖአቸው ነበር፤ ሲነቁ ግን ክብሩንና ከእርሱ ጋር የቆሙትን ሁለት ሰዎች አዩ። [33]ሰዎቹም ከኢየሱስ ተለይተው ሲሄዱ፣ ጴጥሮስ፣ “ጌታ ሆይ፤ እዚህ ብንሆን ለእኛ መልካም ነው፤ ስለዚህ ሦስት ዳስ እንሥራ፤ አንዱ ለአንተ፣

[a]20 ወይም ክርስቶስ

9፥18 ሉቃ3፥21
9፥19 ቍ7፡8፤ ማቴ3፥1
9፥20 ዮሐ1፥49፤ 6፥66-69፤11፥27
9፥21 ማር8፥30
9፥22 ማቴ8፥20፤ 16፥21፤27፥1፡2፤ሐሥ 2፥23፤3፥13
9፥23 ማቴ10፥38፤ ሉቃ14፥27
9፥24 ዮሐ12፥25
9፥26 ማቴ10፥33፤ 16፥27፤ሉቃ12፥9፤2 ጢሞ2፥12
9፥28 ማቴ4፥21፤ ሉቃ3፥21
9፥31 2ጴጥ1፥15
9፥32 ማቴ26፥43
9፥33 ሉቃ5፥5

9፥17 *የተረፈውን ቍርስራሽ እንጀራ ዐሥራ ሁለት መሶብ አነሡ፤* ይህ ድርጊት ማባከን ተገቢ እንዳልሆነ ምሳሌ ከመሆኑም በላይ፣ ተሰብስቦ የነበረው መላው ሕዝብ በሚገባ የተመገበ ለመሆኑ ጕልሕ ማስረጃ ነው (የማር 6፥43 ማብ ይመ)።

9፥18 *ሰዎች እኔን ማን ነው ይሉኛል? ደቀ መዛሙርቱ* ይዘውት የመጡት ወሬ፣ ሄሮድስ ከሰማው ጋር ተመሳሳይ ነው (ቍ 7-8 ይመ)። ይህ ጥያቄ የቀረበው ከሄሮድስ ግዛት ውጭ፣ በቂሣርያ ፊልጶስ አቅራቢያ በስተ ሰሜን በኩል ነው (ማቴ 16፥13 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም የማር 7፥24 ማብ ይመ)።

9፥20 *ጴጥሮስም ... መለሰለት፤* ይህን መልስ የሰጠው ደቀ መዛሙርቱን ሁሉ በመወከል ነው። *የእግዚአብሔር መሲሕ ነህ* የ2፥11 አማራጭ ትርጕም ይመ። በትንቢት የተነገረለት የዚህ መድኅን መምጣት ለረጅም ዘመናት ይጠበቅ ነበር (ዮሐ 4፥25፤ ይመ በተጨማሪም የማቴ 16፥18፤ ማር 8፥29 ማብ ይመ)።

9፥21 *ለማንም እንዳይናገሩ ... አስጠነቀቃቸው፤* ሕዝቡ ስለ መሲሑ ትክክለኛ የሆነ ግንዛቤ ስላልነበራቸው ኢየሱስ ማንነቱን ለሕዝቡ ከመግለጹ በፊት፣ ስለ እርሱ ማንነት በሚገባ ማወቅ ነበረባቸው። ጌታ ዐቢይ የሆነ ዕቅድ ስለ ነበረው፣ ይህ ዕቅዱ በግብታዊነት እንዲደናቀፍ አልፈቀደም (የማቴ 8፥4፤ 16፥20፤ ማር 1፥34 ማብ ይመ)።

9፥22 *የሰው ልጅ፤* የማር 8፥31 ማብ ይመ። *መከራ መቀበል ይገባዋል፤* ሞቱን አስመልክቶ ኢየሱስ እንደሚሞት በግልጽ ሲናገር፣ ይህ የመጀመሪያው ነው (ከዚህ በተጨማሪም ቍ 44፤ 12፥50፤ 17፥25፤ 18፥31-33፤ ይመ ከ24፥7፡25-27 ጋር ያነጻጽሩ)።

9፥23 *መስቀሉንም በየዕለቱ ተሸክሞ፤* ኢየሱስን ለመከተል ራስን መካድ፣ ራስን ሙሉ በሙሉ መስጠትና በሙሉ ፈቃድ መታዘዝ አስፈላጊ ነው፤ ይህም ሳያቋርጥ በተግባር መገለጽ እንዳለበት ሉቃስ በአጽንዖት ገልጾአል፤ “በየዕለቱ” የሚለው ቃል፣ በሌሎቹ ተመሳሳይ ወንጌላት ውስጥ በግልጽ አልተጠቀሰም (ማቴ 16፥24-26፤ ማር 8፥34)። ከገሊላ የመጡት ደቀ መዛሙርቱ በመቶ የሚቈጠሩ ሰዎች በግዛታቸው በመስቀል ሞት ተቀጥተው ስለ ነበር፣ መስቀል ማለት ምን እንደ ሆነ ያውቃሉ።

9፥24 *ነፍሱን ስለ እኔ ብሎ የሚያጠፋት፤* ይህ የኢየሱስ አባባል፣ በአራቱም ወንጌላት ውስጥ የሚገኝ ሲሆን፣ በሁለቱ ወንጌላት ግን ከአንድ ጊዜ በላይ ተጠቅሶ ይገኛል (ማቴ 10፥38-39፤ 16፥24-25፤ ማር 8፥34-35፤ ሉቃ 14፥26-27፤ 17፥33፤ ለየት ባለ መልክም በዮሐ 12፥25ላይ ተጠቅሶአል)። ኢየሱስ ከተናገረው ቃል እንደዚህ ሐሳብ አጽንዖት የተሰጠው የለም።

9፥26 *ማንም... ቢያፍር፤* 12፥9 ይመ፤ በተጨማሪም የማር 8፥38 ማብ ይመ።

*9፥27፤* የማቴ 16፥28 ማብ ይመ። *የእግዚአብሔርን መንግሥት፤* የማቴ 3፥2 ማብ ይመ።

9፥28 *ከስምንት ቀን... በኋላ፤* አንድ ሳምንትን የሚያመለክት ነው (ለምሳሌ በግሪክ ዮሐ 20፥26 ይመ፤ በተጨማሪም (የማቴ 17፥1 ማብ ይመ)። *ጴጥሮስን፣ ዮሐንስንና ያዕቆብን፤* እነዚህ ሦስቱ ደቀ መዛሙርት፣ የኢያኢሮስ ልጅ በተፈወሰችበት ጊዜና (8፥51) በመጨረሻም ኢየሱስ ወደ ጌቴሴማኒ በሄደ ጊዜ ከእርሱ ጋር ነበሩ (ማር 14፥33)። *ወደ አንድ ተራራ፤* የትኛው ተራራ እንደ ሆነ በውል ባይታወቅም፣ በዘልማድ ግን “የታቦር ተራራ” እንደ ሆነ ይነገራል። *ሊጸልይ፤* ሉቃስ አስፈላጊ በሆነ ሁኔታ ውስጥ ጸሎት ያለውን ድርሻ በድጋሚ አመለከተ።

9፥30 *ሙሴና ኤልያስ፤* ሙሴ ታላቁ የብሉይ ኪዳን ነጻ አውጪና ሕግ ሰጪ ሲሆን፣ ኤልያስ ደግሞ ነቢያትን የሚወክል ነው፤ ሙሴ የጀመረውን ሥራ ኢያሱ የፈጸመ ሲሆን፣ ኤልያስ የጀመረው ደግሞ ኤልሳዕ ፈጽሞአል (በሌላ አባባል ኤልሳዕ ማለት ኢያሱ ማለት ነው)። ሙሴና ኤልያስ የጀመሩት ነጻ የማውጣት ሥራ፣ ኢየሱስ ሕዝቡን ከኀጢአት ነጻ በማውጣት ወደ ፍጻሜ ለማድረስ ሊፈጽም ስላለው “ዘፀአት” ይነጋገሩ ነበር (በዕብራይስጥ ኢየሱስ ማለት ኢያሱ ማለት ነው)። የ1ነገ 19፥16 ማብ ይመ።

9፥31 *መለየቱ፤* በግሪኩ “ዘፀአት” ማለት ነው፤ ይህም የኢየሱስ የመስቀል ሞት የተቃረበ መሆኑን የሚያመለክት ነው፤ ምናልባትም የኢየሱስን ሞትና ትንሣኤ፣ እግዚአብሔር ሕዝቡን ከግብፃውያን ነጻ ካወጣበት ሁኔታ ጋር የሚያዛምድ ነው።

9፥32 *እንቅልፍ፤* ሌሊት ስለሆነ ሊሆን ይችላል። *ክብሩንና... አዩ፤* የዘፀ 33፥18 ማብ ይመ።

9፥33 *ሦስት ዳሶች፤* ጊዜያዊ ማረፊያ ሲሆን፣ ሦስቱ

"አንዱ ለሙሴ፣ አንዱም ለኤልያስ ይሆናል" አለው፤ የሚናገረውንም አያውቅም ነበር።

[34]ይህንም እየተናገረ ሳለ ደመና መጥቶ ጋረዳቸው፤ ወደ ደመናውም ሲገቡ ፈሩ። [35]ከደመናውም ውስጥ፣ "የመረጥሁት ልጄ ይህ ነው፤ እርሱን ስሙት" የሚል ድምፅ መጣ። [36]ድምፁም በተሰማ ጊዜ ኢየሱስ ብቻውን ሆኖ ተገኘ፤ ደቀ መዛሙርቱም ነገሩን በልባቸው ያዙ እንጂ፣ ስላዩት ነገር በዚያን ወቅት ለማንም አልተናገሩም።

## ኢየሱስ ርኩስ መንፈስ ያለበትን ልጅ ፈወሰ

9፥37-42፡43-45 ተጓ ምብ – ማቴ17፥14-18፤ 22፡23፤ ማር 9፥14-27፤ 30-32

[37]በማግሥቱ ከተራራው ከወረዱ በኋላ፣ ብዙ ሕዝብ መጥቶ ኢየሱስን አገኘው። [38]በዚህ ጊዜ ከሕዝቡ መካከል አንድ ሰው ድምፁን ከፍ አድርጎ እንዲህ አለ፤ "መምህር ሆይ፤ ያለኝ ልጅ እርሱ ብቻ ስለሆነ ልጄን እንድታይልኝ እለምንሃለሁ። [39]መንፈስ ሲይዘው በድንገት ይጮኻል፤ አረፋ እያስደፈቀው ያንፈራግጠዋል፤ ጕዳትም ካደረሰበት በኋላ በስንት መከራ ይተወዋል፤ [40]ደቀ መዛሙርትህ እንዲያወጡለት ለመንኋቸው፤ ነገር ግን አልቻሉም።"

[41]ኢየሱስም "እምነት የለሽ ጠማማ ትውልድ፤ እስከ መቼ ከእናንተ ጋር እኖራለሁ? እስከ መቼስ እታገሣችኋለሁ? በል ልጅህን ወደዚህ አምጣው" አለ።

[42]ልጁ በመምጣት ላይ ሳለም ጋኔኑ መሬት ላይ ጥሎ አንፈራገጠው፤ ኢየሱስ ግን ርኩሱን[o] መንፈስ ገሥጾ ልጁን ፈወሰው፤ ለአባቱም መልሶ ሰጠው። [43]ሰዎቹም ሁሉ በእግዚአብሔር ታላቅነት ተገረሙ።

እርሱ ባደረገው ሁሉ ሰዎች ሁሉ እየተገረሙ ሳሉ፣ ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን፣ [44]"ይህን የምነግራችሁን ነገር ከቶ እንዳትዘነጉ፤ የሰው ልጅ አልፎ በሰዎች እጅ ይሰጣልና" አለ። [45]እነርሱ ግን ይህን አባባል አልተረዱም፤ እንዳያስተውሉ ነገሩ ተሰውሮባቸው ነበር፤ መልሰው እንዳይጠይቁትም ፈሩ።

## ከሁሉ የሚበልጥ ማን ይሆን?

9፥46-48 ተጓ ምብ – ማቴ 18፥1-5
9፥46-50 ተጓ ምብ - ማቴ 9፥33-40

[46]ከእነርሱ ማን እንደሚበልጥ በደቀ መዛሙርቱ መካከል ክርክር ተነሣ። [47]ኢየሱስም የልባቸውን ሐሳብ ተረድቶ፣ አንድ ሕፃን ይዞ በአጠገቡ አቆመ፤ [48]እንዲህም አላቸው፤ "ይህን ሕፃን በስሜ የሚቀበል ማንም ቢኖር እኔን ይቀበላል፤ እኔን የሚቀበል ደግሞ የላከኝን ይቀበላል፤ ከሁላችሁ የሚያንስ እርሱ ከሁሉ ይበልጣልና።"

[49]ዮሐንስም፣ "ጌታ ሆይ፤ አንድ ሰው በስምህ አጋንንት ሲያወጣ አየን፤ ከእኛ ጋር ሆኖ ስለማይከተል ልንከለክለው ሞከርን" አለው።

[50]ኢየሱስም፣ አትከልክሉት "የማይቃወማችሁ ሁሉ እርሱ ከእናንተ ጋር ነውና" አለው።

## የሰማርያ ሰዎች ተቃውሞ

[51]ኢየሱስ ወደ ሰማይ የሚያርግበት ጊዜ በመቃረቡ፣ ወደ ኢየሩሳሌም ለመሄድ ቈርጦ ተነሣ፤ [52]አስቀድሞም መልእክተኞችን ወደ ዚያ ላከ። እነርሱም ሁኔታዎችን አስቀድመው ሊያመቻቹለት ወደ አንድ የሳምራውያን መንደር ገቡ። [53]ሕዝቡ ግን ወደ ኢየሩሳሌም እየመራ መሆኑን ስላወቁ አልተቀበሉትም። [54]ደቀ መዛሙርቱም ያዕቆብና ዮሐንስ ይህን ሲያዩ፣ "ጌታ ሆይ፤ ኤልያስ እንዳደረገው ሁሉ [p]እሳት ከሰማይ ወርዶ እንዲያጠፋቸው እንድናዝ ትፈቅዳለህን?"

[o]42 ወይም ክፉ
[p]54 አንዳንድ ቅጆች ኤልያስ እንዳደረገው ሁሉ የሚለው የላቸውም

9፥35 ኢሳ42፥1፤ ማቴ3፥17
9፥36 ማቴ17፥9
9፥41 ዘዳ32፥5
9፥44 ቍ22
9፥45 ማር9፥32
9፥46 ሉቃ22፥24
9፥47 ማቴ9፥4
9፥48 ማቴ10፥40፤ ማር9፥35
9፥49 ሉቃ5፥5
9፥50 ማቴ12፥30፤ ሉቃ11፥23
9፥51 ማር16፥19፤ ሉቃ13፥22፤17፥11፤ 18፥31፤19፥28
9፥52 ማቴ10፥5
9፥54 2ነገ1፥10፡ 12፤ማቴ4፥21

ሰዎች፣ ማለትም ሕግ ሰጪው፣ ነቢዩና መሢሑ በእነርሱ ዘንድ እንዲቈዩ አስቦ ይመስላል። ኢየሱስ በቀረው አጭር ጊዜ የጀመረውን ተግባር ፍጻሜ ላይ ማድረስ ስለ ነበረበት፣ ጴጥሮስ የሰነዘረው ሐሳብ ተገቢ አልነበረም (የማር 9፥5 ማብ ይመ)።

9፥35 *የመረጥሁት፤* ወይም "የተመረጠው" ማለት ሲሆን፣ በሙት ባሕር ጥቅልል መጽሐፍ ላይ ከሚገኘው የፓሌስቲና አይሁዳውያን የማዕረግ ስም ጋር ተመሳሳይነት አለው፤ ምናልባትም በኢሳ 42፥1 ላይ የተጻፈውን ሐሳብ ያንጸባርቅ ይሆናል 23፥35 ይመ። *የመረጥሁት ልጄ፤* "የምወደው ልጄ" ከሚለው ጋር ተጓዳኝ ነው (ማቴ 17፥5፤ 2ጴጥ 1፥17 ይመ)።

9፥39 *መንፈስ ሲይዘው፤* ይህ መንፈስ፣ የሚጥል በሽታንና (ማቴ 17፥15) ዲዳነትን (ማር 9፥17) አስከትሎበት ነበር። ክፉ መናፍስት ለልዩ ልዩ በሽታዎች መንሥኤ ነበሩ (የ4፥33 ማብ ይመ)።

*9፥44፤* እየተቃረበ ስላለው የኢየሱስ ሞት የተነገረ ሌላው ትንቢትና (የቍ22 ማብ ይመ)፣ እንዴት እንደሚፈጸምም የሚያመለክት ነው (22፥21 ይመ)።

9፥46 *ማን እንደሚበልጥ፤* ብዙ ጊዜ የተነሣ ጕዳይ ነው (22፥24 ይመ፣ በተጨማሪም ማር 10፥35-45 ይመ)።

9፥48 *ከሁላችሁ የሚያንስ... ከሁሉ ይበልጣልና፤* አንድ ሰው በቅን ልቡና በመመላለስ እግዚአብሔርን ቢያከብር ታላቅ ይሆናል።

9፥49 *ከእኛ ጋር ሆኖ ስለማይከተል፤* ደቀ መዛሙርቱ ባያውቁትም፣ ሰውዬው ከኢየሱስ ጋር ኅብረት ነበረው። (የማር 9፥38 ማብ ይመ)።

9፥50 *የማይቃወማችሁ ሁሉ እርሱ እናንተ ጋር ነውና፤* የሐዋርያትን ድርጊት ከመቃወም አንጻር የተነገረ ነው (ከ11፥23 ጋር ያነጻጽሩ)።

9፥51 *ወደ ኢየሩሳሌም ለመሄድ...ተነሣ፤* በቁሙ፣ ወደ ኢየሩሳሌም ለመሄድ ፊቱን አቀና ማለት ነው (ከኢሳ 50፥7 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ኢየሱስ ተልእኮውን ለመፈጸም ቈርጦ መነሣቱን፣ ሉቃስ በአጽንዖት ገልጿል (የ13፥22 ማብ ይመ)። ወደ ኢየሩሳሌም ያደረገው ይህ ጕዞ ኢየሱስ ወደ መስቀል ሞቱ ያደረገው ጕዞ ባይሆንም፣ በይሁዳ አገልግሎት መጀመሩን ግን ያመለክታል፤ የኢየሩሳሌም ከተማም የዚህ አገልግሎት ማእከል ናት። ዮሐንስ፣ በዳስ በዓል ወቅት ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም ያደረገው ጕዞ እንደ ሆነ በግልጽ የጻፈውን (ዮሐ 7፥1-10)፣ ማርቆስ (10፥1) ወደ ይሁዳ ያደረገው ጕዞ መሆኑን ገልጾአል። በይሁዳ የነበረውን አገልግሎት በ9፥51-13፥21 እና በዮሐ 7፥10-10፥39 ላይ በዝርዝር ተገልጾአል።

9፥52 *የሳምራውያን መንደር፤* ሳምራውያን፣ በኢየሩሳሌም የሃይማኖት በዓል ለማክበር ጕዞ በሚያደርጉት አይሁዳውያን ላይ ጥላቻ ነበራቸው። ከገሊላ በሰማርያ በኩል ወደ ኢየሩሳሌም ለመድረስ ቢያንስ ሦስት ቀን ይወስድ ነበር፤ ይህም ሆኖ ሳለ ሳምራውያን መንገደኞችን ለአንድ ቀን እንኳ ለማሳረፍ ፈቃደኞች አይደሉም፤ ከዚህ ጥላቻቸው የተነሣም፣ ከገሊላ ወደ ኢየሩሳሌም የሚጓዙ አይሁዳውያን አብዛኛውን ጊዜ የሚጓዙት ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተ ምሥራቅ በኩል ነበር።

9፥54 *እሳት... ወርዶ፤* ኤልያስ እንዳደረገው ማለት ነው (2ነገ 1፥9-16)። *ያዕቆብና ዮሐንስ* "የነጐድጓድ ልጆች" ይባሉ ነበር (ማር 3፥17)።

አሉት:: [55]ኢየሱስ ግን ዘወር ብሎ ገሠጻቸውና[w] "እናንተ ከምን ዐይነት መንፈስ እንደ ሆናችሁ አታውቁም፤ የሰው ልጅ የመጣው የሰውን ሕይወት ለማዳን ነው እንጂ ለማ ጥፋት አይደለምና" አላቸው [56]ወደ ሌላ መን ደርም ሄዱ::

## ደቀ መዝሙርነት የሚያስከፍለው ዋጋ

9፥57-60 ተጓ ምብ – ማቴ 8፥19-22

[57]በመንገድ ሲሄዱም አንድ ሰው ቀርቦ፣ "ወደምትሄድበት ሁሉ እከተልሃለሁ" አለው::

[58]ኢየሱስም፣ "ቀበሮዎች ጕድጓድ፣ የሰማይ ወፎችም ጎጆ አላቸው፤ የሰው ልጅ ግን ዐንገቱን እንኳ የሚያስገባበት የለውም" አለው::

[59]ሌላውን ሰው ግን፣ "ተከተለኝ" አለው::

ሰውየውም፣ "ጌታ ሆይ፤ አስቀድሜ ልሂድና አባቴን ልቅበር" አለው::

[60]ኢየሱስም፣ "ሙታን ሙታናቸውን እንዲቀብሩ ተዋቸው፤ አንተ ግን ሄደህ የእግዚአብሔርን *መንግሥት* ስበክ" አለው::

[61]ሌላ ሰው ደግሞ፣ "ጌታ ሆይ፤ መከተል እከተልሃለሁ፤ ነገር ግን ልመለስና መጀመሪያ የቤቴን ሰዎች እንድሰናበት ፍቀድልኝ" አለ::

[62]ኢየሱስ ግን፣ "ዕርፍ ጨብጦ ወደ ኋላ የሚመለከት ሰው ለእግዚአብሔር *መንግሥት* የተገባ አይደለም" አለው::

## ኢየሱስ ሰባ ሁለቱን ላካቸው

10፥4-12 ተጓ ምብ - ሉቃ 9፥3-5
10፥13-15፡21፡22 ተጓ ምብ – ማቴ 11፥21-23፡25-27
10፥23፡24 ተጓ ምብ -ማቴ 13፥16፡17

**10** ከዚህ በኋላ ጌታ ሌሎች ሰባ ሁለት ሰዎችን መርጦ ሾመ፤ ወደሚሄድበትም ከተማና ቦታ ሁሉ እንዲቀድሙት፣ ሁለት ሁለት አድርጎ ላካቸው፤ [2]እንዲህም አላቸው፤ "*መ*ከሩ ብዙ ነው፤ ሠራተኞች ግን ጥቂት ናቸው፤ ስለዚህ የመከሩ ጌታ ሠራተኞችን ወደ መከሩ ቦታ እንዲልክ ለምኑት:: [3]እንግዲህ ሂዱ፤ እንደ በጎች በተኵላዎች መካከል እልካችኋለሁ:: [4]ኰረጆ ወይም ከረጢት፣ ወይም ጫማ አትያዙ፤ በመንገድ ላይም ለማንም ሰላምታ አትስጡ::

[5]"ወደ ማንኛውም ቤት ስትገቡ አስቀድማችሁ፣ ሰላም ለዚህ ቤት ይሁን በሉ፤ [6]የሰላም ሰው በዚያ ካለ፣ ሰላማችሁ ያርፍበታል፤ አለዚያም ሰላማችሁ ለእናንተው ይመለሳል:: [7]ያቀረቡላችሁን ሁሉ እየበላችሁና እየጠጣችሁ በዚያ ቤት ተቀመጡ፤ የሚሠራ ደመወዝ ማግኘት ይገባዋልና:: ከአንዱ ቤት ወደ ሌላው ቤት አትዘዋወሩ::

[8]"ወደ ማንኛውም ከተማ ስትገቡ ሰዎቹ ከተቀበሏችሁ፣ ያቀረቡላችሁን ብሉ:: [9]በዚያ የሚገኙትን በሽተኞች እየፈወሳችሁ፣ 'የእግዚአብሔር *መንግሥት* ወደ እናንተ ቀርባለች' በሏቸው:: [10]ነገር ግን ወደ አንድ ከተማ ገብታችሁ ካልተቀበሏችሁ፣ ወደ አደባባዩ ውጡና እንዲህ በሉ፤ [11]'በእግራችን ላይ ያለውን የከተማችሁን ትቢያ እንኳ እናራግፍላችኋለን፤ ነገር ግን የእግዚአብሔር *መንግሥት* እንደ ቀረበች ይህን ዕወቁ::' [12]እላችኋለሁ፤ በዚያን ዕለት ከዚያች ከተማ ይልቅ ለሰዶም ቀላል ይሆንላታል::

[13]"ወዮልሽ ኮራዚን! ወዮልሽ ቤተ ሳይዳ! በእናንተ የተደረገው ታምራት በጢሮስና በሲዶና ተደርጎ ቢሆን ኖሮ፣ ገና ዱሮ ማቅ ለብሰው፣ ዐመድ ነስንሰው ንስሓ በገቡ ነበር:: [14]ነገር ግን በፍርድ ጊዜ ከእናንተ ይልቅ ለጢሮስና ለሲዶና ይቀልላቸዋል:: [15]አንቺም ቅፍርናሆም፣ ወደ ሰማይ ከፍ ከፍ አልሽን? ወደ ሲኦል[e] ትወርጃለሽ::

9፥58 ማቴ8፥20
9፥59 ማቴ4፥19
9፥60 ማቴ3፥2
9፥61 1ነገ19፥20
10፥1 ማቴ10፥1፤ ማር6፥7፤ሉቃ7፥13፤ 9፥1፡2፡51፡52
10፥2 ማቴ9፥37፡ 38፤ዮሐ4፥35
10፥3 ማቴ10፥16
10፥7 1ጢሞ5፥18
10፥8 1ቆሮ10፥27
10፥9 ማቴ3፥2
10፥11 ቍ9፤ ማቴ10፥14
10፥12 ማቴ10፥ 15፤ማቴ11፥24
10፥13 ሉቃ6፥24- 26፤ራእ11፥3
10፥15 ማቴ4፥13

[w]55 56 አንዳንድ ቅጆች *ገሠጻቸው፤ [56]ከዚያም ወደ ሌላ መንደር ሄዱ* ይላሉ::
በቍ 55 ላይ በትእምርተ ጥቅሱ ውስጥ የሚገኘው ዐረፍተ ነገር ተአማኒ በሆኑ ብዙ የጥንት ቅጆች ላይ አይገኝም::
[e]15 ወይም *ወደ ጥልቁ*

9፥55 *ገሠጻቸው፤* የ2ነገ 1፥10 ማብ ይመ::

9፥57 *ሲሄዱም፤* በሰማርያ አድርገው ወደ ኢየሩሳሌም በመጓዝ ላይ እንዳሉ ማለት ነው::

9፥59 *አባቴን ልቅበር፤* በዚህ ጊዜ አባትየው ሞቶ ቢሆን ኖሮ፣ ይህ ሰው የሚገኘው በቀብር ሥርዐቱ ላይ ነበር፤ ነገር ግን ሰውየው መቈየት የፈለገው አባቱ እስኪሞት ድረስ እንደ ሆነ ግልጽ ነው፤ ይህ ደግሞ ዓመታት ሊቈይ ይችላል:: በመንፈስ ሙታን የሆኑ፣ በሥጋ ሙት የሆኑትን ሊቀብሩ እንደሚችሉና በመንፈስ ሕያው የሆኑ ግን፣ የእግዚአብሔርን መንግሥት በማወጅ ተግባር ሊጠመዱ እንደሚገባቸው ነገረው::

10፥1 *ሰባ ሁለት ሰዎችን መርጦ ሾመ፤* ቍጥራቸው የተገለጸው በዚህ ወንጌል ውስጥ ብቻ ቢሆንም፣ ተመሳሳይ ትእዛዝ ግን ለዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያትም ተሰጥቶአል (ማቴ 9፥37-38፤ 10፥7-16፤ ማር 6፥7-11 ይመ፤ ከሉቃ 9፥3-5 ጋር ያነጻጽሩ)፤ በጥንት ቅጆች የሚገኘው አንዳንድ ልዩነት፣ የተሾሙት ሰዎች ቍጥር 72 ይሁኑ 70 ግልጽ አይደለም (አማራጭ ትርጕሙን ይመ):: ጌታ ኢየሱስ በትምህርቱ ገሊላን እንዳዳረሰ ሁሉ ይሁዳንም አዳርሶአል (የ9፥51 ማብ ይመ):: *ሁለት ሁለት፤* በገሊላ አገልግሎቱ ወቅትም ኢየሱስ ሐዋርያቱን ሁለት ሁለት አድርጎ ልኮአቸዋል (9፥1-6፤ ማር 6፥7 እና ማብ ይመ)፤ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያንም ይኸው ልምድ ይሠራበች ነበር (ሐሥ 13፥2፤ 15፥27፡39-40፤ 17፥14፤ 19፥22)::

10፥4 *ኰሮጆ ወይም ከረጢት፣ ወይም ጫማ አትያዙ፤* የገንዘብ ቦርሳ፣ የልብስ ሻንጣ ወይም ትርፍ ጫማ ሳይዙ ቀለል ያለ ነገር ይዘው መጓዝ ነበረባቸው:: *ሰላምታ አትስጡ፤* በመንገድ ላይ ወደሚገኘው መንደር ጎራ ማለትና ለሚያጋጥሙአቸው ሰዎች ሁሉ የተለመደውን ረጅም ሰላምታ ማቅረብ አልነበረባቸውም፤ ምክንያቱም የተሰጣቸው ተልእኮ አስቸኳይ ነበር::

10፥7 *አትዘዋወሩ፤* የ9፥4 ማብ ይመ::

10፥9 *የእግዚአብሔር መንግሥት ... ቀርባለች፤* የኢየሱስ መልእክት ዋና ሐሳብ ነው (የ4፥43፤ ማቴ 3፥2 ማብ ይመ)::

10፥11 *ትቢያ... እናራግፍላችኋለን፤* የ9፥5 ማብ ይመ::

10፥12 *በዚያን ዕለት፤* የፍርድ ቀን ማለት ነው:: *ለሰዶም ቀላል ይሆንላታል፤* የሰዶም ኀጢአት እጅግ ስለ በዛ እግዚአብሔር ቢያጠፋትም (ዘፍ 19፥24-28፤ ይሁ 7)፣ የኢየሱስና የደቀ መዛሙርቱን መልእክት የሰሙ ሰዎች የእግዚአብሔር መንግሥት ወንጌል ስለ ተሰበከላቸው፣ ከሰዶም ሰዎች የበለጠ ተጠያቂ ናቸው::

10፥13 *ኮራዚን... ቤተ ሳይዳ፤* የማቴ 11፥21 ማብ ይመ::

10፥14 *ለጢሮስና ለሲዶና፤* ከገሊላ በስተ ሰሜን በፊንቄ የሚገኙ የአሕዛብ ከተሞች ሲሆኑ፣ እንደ አብዛኛው የገሊላ ሕዝብ የኢየሱስን ታምራት ለማየትና ስብከቱን ለመስማት ዕድል አላገኙም (የቍ12 ማብ ይመ)::

10፥15 *ቅፍርናሆም፤* በገሊላ ባሕር በሰሜን ዳርቻ የምትገኝ የኢየሱስ አገልግሎት ማእከል ከተማ ስትሆን (ማቴ 4፥13 እና ማብ ይመ)፣ ነዋሪዎቿዋም ኢየሱስን ለማየትና ለመስማት ሰፊ ዕድል ነበራቸው፤ ከዚህ የተነሣም ለእምቢተኝነታቸው የሚደርስባቸው ፍርድ የባሰ ነበር::

[16]“እናንተን የሚሰማ እኔን ይሰማል፤ እናንተን የማይቀበል እኔን አይቀበልም፤ እኔንም የማይቀበል የላከኝን አይቀበልም።”

[17]ሰባ ሁለቱም ደስ እያላቸው ተመልሰው፣ “ጌታ ሆይ፤ አጋንንት እንኳ በስምህ ተገዙልን” አሉት።

[18]እርሱም እንዲህ አላቸው፤ “ሰይጣን እንደ መብረቅ ከሰማይ ሲወድቅ አየሁ። [19]እንግዲህ እባቡንና ጊንጡን እንድትረግጡ፣ በጠላትም ኀይል ሁሉ ላይ ሥልጣን ሰጥቻችኋለሁ፤ የሚጐዳችሁም አንዳች ነገር አይኖርም። [20]ይሁን እንጂ መናፍስት ስለ ተገዙላችሁ በዚያ ደስ አይበላችሁ፤ ስማችሁ ግን በሰማይ ስለ ተጻፈ ደስ ይበላችሁ።”

[21]በዚያን ጊዜ ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስ ሐሤት አድርጎ እንዲህ አለ፤ “የሰማይና የምድር ጌታ፤ አባት ሆይ፤ ይህን ሁሉ ከጥበበኞችና ከዐዋቂዎች ሰውረህ ለሕፃናት ስለ ገለጥህላቸው አመሰግንሃለሁ፤ አዎን፣ አባት ሆይ፤ ይህ የአንተ በጎ ፈቃድ ሆኖአልና።

[22]“ሁሉ ከአባቴ ዘንድ ተሰጥቶኛል፤ ደግሞም ወልድ ማን እንደ ሆነ ከአብ በቀር የሚያውቅ የለም፤ አብ ማን እንደ ሆነም ከወልድ በቀር፣ ወልድም ሊገልጥለት ከሚፈቅደው በቀር የሚያውቅ የለም።”

[23]ወደ ደቀ መዛሙርቱም ዘወር ብሎ ለብቻቸው እንዲህ አላቸው፤ “እናንተ የምታዩትን የሚያዩ ዐይኖች ብፁዓን ናቸው፤ [24]እላችኋለሁና፤ ብዙ ነቢያትና ነገሥታት እናንተ የምታዩትን ለማየት ፈልገው አላዩም፤ የምትሰሙትንም ለመስማት ፈልገው አልሰሙም።”

## ደጉ ሳምራዊ

10፥25-28 ተጓ ምብ - ማቴ 23፥34-40፤ ማር 12፥28-31

[25]እነሆም አንድ ቀን፣ አንድ ሕግ ዐዋቂ ኢየሱስን ሊፈትነው ተነሥቶ፣ “መምህር ሆይ፤ የዘላለምን ሕይወት ለመውረስ ምን ላድርግ?” አለው።

[26]ኢየሱስም፣ “በሕግ የተጻፈው ምንድን ነው? እንዴትስ ታነበዋለህ?” ሲል መለሰለት።

[27]ሰውየውም መልሶ፣ “ ‘ጌታ አምላክህን በፍጹም ልብህ፣ በፍጹም ነፍስህ፣ በፍጹም ኀይልህና በፍጹም ሐሳብህ ውደድ፤ ባልንጀራህንም እንደ ራስህ ውደድ’ ይላል” አለው።

[28]ኢየሱስም፣ “በትክክል መልሰሃል፤ አንተም እንደዚሁ አድርግ፤ በሕይወት ትኖራለህ” አለው።

[29]ሰውየውም ራሱን ጻድቅ ለማድረግ ፈልጎ፣ “ለመሆኑ ባልንጀራዬ ማን ነው?” አለው።

[30]ኢየሱስም እንዲህ ሲል መልስ ሰጠው፤ “አንድ ሰው ከኢየሩሳሌም ወደ ኢያሪኮ ሲወርድ በወንበዴዎች እጅ ወደቀ፤ ልብሱንም ገፈው ደበደቡት፤ በሞት አፋፍ ላይ ጥለውት ሄዱ። [31]አንድ ካህን በአጋጣሚ በዚያው መንገድ ቍልቍል ሲወርድ አየውና ገለል ብሎ አለፈ። [32]ደግሞም አንድ ሌዋዊ እዚያ ቦታ ሲደርስ አየውና እርሱም ገለል ብሎ አለፈ። [33]አንድ ሳምራዊ ግን እግረ መንገዱን ሲሄድ ሰውየው ወዳለበት ቦታ ደረሰ፤ ባየውም ጊዜ ዐዘነለት፤ [34]ቀርቦም ቍስሎቹ ላይ ዘይትና የወይን ጠጅ አፍስሶ አሰረለት፤ በራሱም አህያ ላይ አስቀምጦት ወደ እንግዶች ማረፊያ ቤት ወስዶ፤ በዚያም ተንከባከበው። [35]በማግሥቱም ሁለት ዲናር[ቿ] አውጥቶ ለማረፊያ ቤቱ ባለቤት ሰጠና፣ ‘ይህን ሰው ዐደራ አስታመው፤ ከዚህ በላይ የምታወጣውንም ወጪ እኔ ስመለስ እከፍልሃለሁ’ አለው።

[36]“እንግዲህ፣ ከእነዚህ ከሦስቱ በወንበዴዎች እጅ ለወደቀው ሰው ባልንጀራ የሆነው የትኛው ይመስልሃል?”

[ቿ]35 ወይም ሁለት የናስ ሳንቲሞች

10፥16 ማቴ10፥40
10፥17 ቍ1፤ ማር16፥17
10፥18 ኢሳ 14፥12፤ማቴ4፥10፤ ራእ9፥1፤12፥8፡9
10፥19 ማር 16፥18፤ሐሥ28፥3-5
10፥20 ራእ20፥12
10፥21 1ቆሮ 1፥26-29
10፥22 ማቴ28፥18፤ ዮሐ1፥18
10፥24 1ጴጥ 1፥10-12
10፥25 ማቴ19፥16፤ ሉቃ18፥18
10፥27 ዘሌ19፥18፤ ዘዳ6፥5፤ማቴ5፥43
10፥28 ሮሜ7፥10
10፥29 ሉቃ16፥15
10፥31 ዘሌ21፥1-3
10፥33 ማቴ10፥5

10፥18 *ሰይጣን ... ሲወድቅ፤* አጋንንትን እንኳ፣ ደቀ መዛሙርቱ በተቀበሉት ሥልጣን ያወጡ ስለ ነበር (ቍ 17)፣ ይህ ሁኔታ ሰይጣን እንደ ተሸነፈ ያሳያል።

10፥19 *እባቡንና ጊንጡን ... በጠላትም ኀይል፤* እባብና ጊንጥ ክፉ መናፍስትን የሚያመለክቱ ሲሆን፣ “ጠላት” የተባለው ደግሞ ሰይጣን ነው።

*10፥20፤* የሰው ድነት ክፉውን ከማሸነፍ ወይም ከሚያመጣው ጕዳት ከማምለጥ ይበልጣል። *ስማችሁ... ስለ ተጻፈ፤* ሰው ድነት ሲቀበል፣ ስሙ በሰማይ መዝገብ ይጻፋል (መዝ 69፥28፤ ዳን 12፥1፤ ፊል 4፥3፤ ዕብ 12፥23፤ ራእ 3፥5 ይመ)።

10፥25 *ሕግ ዐዋቂ፤* በቅዱሳት መጻሕፍት ጥልቅ ዕውቀት ያለው ምሁር ተራ ጥያቄ መጠየቁ (18፥18፤ ከማቴ 22፥35 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ከኢየሱስ ጋር የመወያያ ሐሳብ ለማግኘት ወይም ኢየሱስ ምን ዐይነት አስተማሪ እንደ ሆነ ለማወቅ ፈልጎ ሊሆን ይችላል፤ የ7፥30 ማብ ይመ።

10፥27 *አምላክህን... ውደድ፤ ባልንጀራህንም ... ውደድ፤* ኢየሱስ፣ በሌላ ስፍራም የቀረበለትን ጥያቄዎች ለመመለስ (ማቴ22፥35-40፤ ማር12፥ 28-32)፣ ተመሳሳይ የሆኑትን እነዚህን ሁለት የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍሎች (ዘዳ 6፥5፤ ዘሌ 19፥18)፣ በአንድ ላይ በማጣመር ተጠቅሞባቸዋል። በአራት መልክ የተገለጸው ፍቅርም ሆነ (ልብ፣ ነፍስ፣ ኀይል፣ ሐሳብ በማለት እዚህ ላይና በማር 12፥30 ላይ የተጠቀሰው) በሦስት መልክ የተገለጸው ፍቅር (ዘዳ 6፥5፤ ማቴ 22፥37፤ ማር 12፥33)፣ የሚፈለገው ዐቢይ ጕዳይ፣ በሙሉ ልብ መትጋት ነው።

10፥29 *ራሱን ጻድቅ ለማድረግ፤* ሰውዬው ላቀረበው የመጀመሪያ ጥያቄ የተሰጠው መልስ የሚያውቀው ነው፤ ለመመስገን ፈልጎም እንዲብራራለት ጠየቀ፤ ያቀረበውም ጥያቄ “ባልንጀራዬ ማን ነው?” የሚል ነበር።

10፥30 *ከኢየሩሳሌም ወደ ኢያሪኮ፤* 27 ኪ.ሜ. ያህል ነው፤ ኢየሩሳሌም ከባሕር ወለል በላይ 2500 ጫማ በላይ ስትሆን (762 ሜትር ያህል)፣ ኢያሪኮ ግን ከባሕር ወለል 800 ጫማ በታች ትገኛለች (243 ሜትር ያህል)። መንገዱ ቋጥኝ የበዛበት በረሓማ ስለ ሆነ፣ ለዘራፊዎች አመቺ ነበር።

10፥31-33 *ካህን ... ሌዋዊ ... ሳምራዊ፤* ኢየሱስ ያመሰገነው የሃይማኖት መሪውን ወይም መለስተኛ ኀላፊነት የነበረውን ሰው ሳይሆን፣ የተናቀውንና ባይተዋር የሆነውን ሰው እንደ ሆነ ማስተዋል ተገቢ ነው፤ አይሁዳውያን ሳምራውያንን ዲቃላና (የማቴ 10፥5 ማብ ይመ) በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ስንኩላ ናቸው ብለው ይንቁአቸው ነበር (የዮሐ 4፥20-22 ማብ ይመ)። ሳምራውያንና አይሁዳውያን ግልጽ የሆነ የእርስ በርስ ጥላቻ ቢኖራቸውም፣ ኢየሱስ ግን ፍቅር በብሔራዊ ድንበር እንደማይወሰን በአጽንዖት ገለጸ።

10፥35 *ሁለት ዲናር፤* በዚያን ዘመን፣ የሁለት ቀን ደመወዝ ሲሆን፣ ይህም አንድን ሰው ለሁለት ወር ያህል በመለስተኛ ሆቴል ሊያቈየው ይችል ነበር።

10፥36 *ለወደቀው ሰው ባልንጀራ የሆነው የትኛው ይመስልሃል?* ጥያቄው “በተግባር መልካም ወዳጅ መሆኑን ያረጋገጠው ማን ነው?” የሚል ነው።

[37]ሕግ ዐዋቂውም፣ “የራራለት ነዋ” አለ። ኢየሱስም፣ “አንተም ሂድና እንዲሁ አድርግ” አለው።

## ኢየሱስ በማርታና በማርያም ቤት

[38]ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱ መንገድ ሲሄዱ፣ ኢየሱስ ወደ አንድ መንደር ገባ፤ ማርታ የተባለች አንዲት ሴትም በቤቷ ተቀበለ ችው። [39]እርሷም ማርያም የተባለች እኅት ነበረቻት፤ ማርያምም ቃሉን እየሰማች በጌታ እግር ሥር ተቀምጣ ነበር። [40]ማርታ ግን በሥራ ብዛት ትባክን ነበርና ወደ እርሱ ቀርባ፣ “ጌታ ሆይ፤ እኅቴ ሥራውን ለእኔ ብቻ ጥላ ስትቀመጥ ዝም ትላለህን? እንድታግዘኝ ንገራት እንጂ” አለችው።

[41]ጌታ ግን እንዲህ ሲል መለሰላት፤ “ማርታ፣ ማርታ፤ ስለ ብዙ ነገር ትጨነቂያለሽ፤ ትዋከቢ አለሽም፤ [42]የሚያስፈልገው ግን አንድ ነገር ብቻ ነው[ገ]፤ ማርያም እኮ የሚሻለውን ድርሻ መርጣለች፤ ይህም ከእርሷ አይወሰድም።”

## ኢየሱስ ያስተማረው ጸሎት

11፥2-4 ተጓ ምብ – ማቴ 6፥9-13
11፥9-13 ተጓ ምብ – ማቴ 7፥7-11

**11** አንድ ቀን ኢየሱስ በአንድ ስፍራ ይጸልይ ነበር፤ ጸሎቱንም እንደ ጨረሰ፣ ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ፣ “ጌታ ሆይ፤ ዮሐንስ ደቀ መዛሙርቱን ጸሎት እንዳስተማራቸው አንተም መጸለይን አስተምረን” አለው።

[2]እርሱም እንዲህ አላቸው፤ “ስትጸልዩ እንዲህ በሉ፤

“አባታችን[ጠ] ሆይ፤
ስምህ ይቀደስ፤
መንግሥትህ ትምጣ፤[ጨ]
[3]የዕለት እንጀራችንን በየዕለቱ ስጠን፤
[4]በደላችንን ይቅር በለን፤
እኛም የበደሉንን[ጰ] ሁሉ
ይቅር ብለናልና።
ወደ ፈተናም አታግባን።”[ጸ]

[5]ደግሞም እንዲህ አላቸው፤ “ከእናንተ አንዱ ወዳጅ ቢኖረውና በእኩለ ሌሊት ወደ እርሱ ሄዶ፣ “ወዳጄ ሆይ፤ ሦስት እንጀራ አበድረኝ፤ [6]አንድ ባልንጀራዬ ከመንገድ መጥቶብኝ የማቀርብለት ምንም ነገር የለኝምና” ብሎ ለመነው እንበል።

[7]“በቤት ውስጥ ያለውም፣ “አታስቸግረኝ፤ በሩ ተቈልፎአል፤ ልጆቼም አብረውኝ ተኝተዋል፤ ከእንግዲህ ተነሥቼ ልሰጥህ አልችልም” ይለዋልን? [8]እላችኋለሁ፤ ወዳጁ በመሆኑ ተነሥቶ ባይሰጠው እንኳ፣ ስለ ንዝነዛው[ፀ] ብቻ የሚፈልገውን ሁሉ ይሰጠዋል።

[9]“ስለዚህ እላችኋለሁ፤ ለምኑ ይሰጣችኋል፤ ፈልጉ ታገኛላችሁ፤ በር አንኳኩ ይከፈትላችኋል፤ [10]ምክንያቱም የሚለምን ሁሉ ይቀበላል፤ የሚፈልግም ያገኛል፤ በር ለሚያንኳኳም ይከፈትለታል።

[11]“ከእናንተ መካከል አባት ሆኖ ሳለ ልጁ[ፈ] ዓሣ ቢለምነው እባብ የሚሰጠው ይኖራልን? [12]ወይስ ዕንቍላል ቢለምነው ጊንጥ ይሰጠዋልን? [13]እናንተ ክፉዎች ሆናችሁ ሳላችሁ፣ ለልጆቻችሁ መልካም ስጦታን መስጠት ካወቃችሁበት፣ የሰማዩ አባታችሁ ታዲያ ለሚለምኑት መንፈስ ቅዱስን እንዴት አብልጦ አይሰጥ!”

## ጌታ ኢየሱስና ብዔል ዜቡል

11፥14፡15፤17-22፤ 24-26 ተጓ ምብ - ማቴ12፥22:24-29፤ 43-45
11፥17-22 ተጓ ምብ – ማር 3፥23-37

[14]አንድ ቀን ኢየሱስ ድዳ ጋኔን ያወጣ ነበር፤ ጋኔኑም ከወጣለት በኋላ ድዳው ሰው ተናገረ፤ ሕዝቡም ተገረመ። [15]አንዳንዶቹ ግን፣ “በአጋንንት አለቃ፣ በብዔል ዜቡል[ፐ]፣ አጋንንትን ያወጣል” አሉ፤ [16]አንዳንዶቹ ደግሞ ሊፈታተኑት ከሰማይ ምልክት እንዲያሳያቸው ከእርሱ ይፈልጉ ነበር።

10፥38 ዮሐ11፥1፤ 12፥2
10፥39 ሉቃ8፥35፤ ዮሐ11፥1፤12፥3
10፥40 ማር4፥38
10፥41 ማቴ6፥25-34፤ሉቃ12፥11:22
10፥42 መዝ27፥4
11፥1 ሉቃ3፥21፤ ዮሐ13፥13
11፥2 ማቴ3፥2
11፥4 ማቴ18፥35፤ 26፥41፤ማር11፥25፤ ያዕ1፥13
11፥8 ሉቃ18፥1-6
11፥9 ማቴ7፥7
11፥14ማቴ፥32:33
11፥15 ማቴ9፥34፤ ማር3፥22
11፥16 ማቴ12፥38

[ገ]42 አንዳንድ ቅጆች *የሚያስፈልገው ግን ጥቂት ብቻ ነው* ይላሉ
[ጠ]2 አንዳንድ ቅጆች *በሰማይ የምትኖር አባታችን* ይላሉ
[ጨ]2 አንዳንድ ቅጆች *ፈቃድህ በሰማይ እንደ ሆነች እንዲሁ በምድር ትሁን* ይላሉ
[ጰ]4 አንዳንድ ቅጆች *በእኛ ላይ ኀጢአት የሠሩትን* ይላሉ።
[ጸ]4 አንዳንድ ቅጆች *ከክፉው ግን አድነን* ይላሉ
[ፀ]8 ወይም *ስለ ብዙ ልመናው*
[ፈ]11 አንዳንድ ቅጆች *ዳቦ ቢለምነው ድንጋይ የሚሰጠው አለን?* የሚል አላቸው።
[ፐ]15 ግሪኩ *ብዔዜቡል* ወይም *ብዔል ዜብል* ይላል፤ እንዲሁም ቍ18:19 *ይመ*

10፥38 *መንደር፤* ከኢየሩሳሌም 3ኪ.ሜ. ያህል ርቃ የምትገኘውን ቢታንያን የሚያመለክት ሲሆን፣ የማርያምና የማርታ መኖሪያ ናት (ዮሐ 12፥1-3)።

11፥1 *ኢየሱስ... ይጸልይ ነበር፤* ኢየሱስ የሚጸልየው፣ ልዩ ነገር ሲያጋጥመው ብቻ ሳይሆን (ለምሳሌ ሲጠመቅ 3፥21፤ ዐሥራ ሁለቱን ሲመርጥ 6፥12፤ በጌቴሴማኒ 22፥41)፣ ዘወትርም ነበር *መጸለይን አስተምረን፤* ጌታ ያስተማረው ጸሎት፣ ለቀረበው ጥያቄ መልስ ሆኖ ተሰጥቶአል፤ ይህ ጸሎት በተራራው ስብከት ላይም የሚገኝና (ማቴ 6፥9-13)፣ ከዚያም ጋር ተመሳሳይ ነው። ማቴዎስ፣ ስለ ጸሎት በተራራው ስብከት በጻፈው ውስጥ፣ የመጨረሻዎቹን ሁለት ልመናዎች በማጣመር ስድስት ልመናዎችን የጠቀሰ ሲሆን፣ ሉቃስ ግን ስለ ጸሎት በጻፈው ውስጥ አምስት ልመናዎች ጠቅሶአል።

11፥4 *በደላችንን ይቅር በለን፤* ማቴ 6፥12 ላይ “ዕዳችንን” የሚል ሐሳብ አለው፤ ይሁን እንጂ ትርጒሙ “ኀጢአታችንን” ማለት ነው። ኢየሱስ ይህን እውነት በሌላም ጊዜ አስተምሮታል (ማቴ 18፥35፤ ማር 11፥25)። ይህን ጸሎት አማኞች ዘወትር ሊጸልዩት የሚገባ ነው፤ ከእግዚአብሔር ጋር የተቋረጠውን ግንኙነት ለማደስ በየዕለቱ ይቅርታን ማግኘት አስፈላጊ ነው።

*11፥5-13፤* ኢየሱስ በጸሎት መትጋት አስፈላጊ እንደ ሆነ (ቍ5-8)፣ እግዚአብሔርም ጸሎትን እንደሚመልስ ማረጋገጫ ሰጠ (ቍ9-13)። የትምህርቱ አቀራረብ ሂደትም ከትንሽ ወደ ትልቅ ነው (ቍ13 ይመ)።

11፥13 *መንፈስ ቅዱስን እንዴት... አይሰጥ!፤* ማቴ 7፥11 ላይ “መልካም ስጦታዎች” ይላል፤ ይኸውም መንፈሳዊ ስጦታዎች ማለት ነው፤ ሉቃስ የእግዚአብሔር ታላቅ ስጦታ በሆነው በመንፈስ ቅዱስ ሥራ ላይ አጽንዖት ሰጥቶአል።

11፥14 *ድዳ ጋኔን፤* የ4፥33 ማብ ይመ። ይህ ክፉ መንፈስ ድዳ ያደርጋል። በማቴዎስ 12፥22-30 ላይ የሚገኘው ተጓዳኝ ክፍል ይህ ሰው ዐይነ ስውርም እንደ ሆነ ያመለክታል (ማር 3፥20-27 ይመ)።

11፥15 *በአጋንንት አለቃ፣ በብዔል ዜቡል፤* ሰይጣን ማለት ነው (ቍ 18)፤ የማቴ 10፥25 ማብ ይመ።

11፥16 *ከሰማይ ምልክት፤* ኢየሱስ ድዳውን መፈወሱ ምልክት ሆኖላቸው ሳለ፣ ለመቀበል ግን አልፈለጉም።

[17]ኢየሱስ ግን ሐሳባቸውን ዐውቆ እንዲህ አላቸው፤ “እርስ በርሱ የሚከፋፈል መንግሥት ሁሉ ይጠፋል፤ የሚለያይ ቤትም ይወድቃል:: [18]ሰይጣንም እርስ በርሱ ከተከፋፈለ፣ መንግሥቱ እንዴት ይጸናል? አጋንንትን በብዔል ዜቡል እንደማወጣ ትናገራላችሁና:: [19]እንግዲህ እኔ አጋንንትን የማወጣው በብዔል ዜቡል ከሆነ፣ ልጆቻችሁ በማን ያወጧቸው ይሆን? ስለዚህ እነርሱ ፈራጆች ይሆኑባችኋል:: [20]እኔ ግን አጋንንትን የማወጣው በእግዚአብሔር ጣት ከሆነ፣ የእግዚአብሔር መንግሥት ወደ እናንተ እንደ መጣች ዕወቁ::

[21]“ብርቱ ሰው በሚገባ ታጥቆ ቤቱን ከጠበቀ፣ ንብረቱ በሰላም ይቀመጣል:: [22]ነገር ግን ይበልጥ ብርቱ የሆነ ሰው መጥቶ ካጠቃውና ካሸነፈው ታምኖበት የነበረውን ትጥቁን ያስፈታዋል፤ ምርኮውንም ወስዶ ለሌሎች ያካፍላል::

[23]“ከእኔ ጋር ያልሆነ ይቃወመኛል፤ ከእኔ ጋር የማይሰበስብም ይበትናል::

[24]“ርኩስ [u]መንፈስ ከሰው ሲወጣ ዕረፍት ፍለጋ ውሃ በሌለበት ስፍራ ይንከራተታል፤ ሳያገኝም ሲቀር፣ ወደ ወጣሁበት ቤቴ እመለሳለሁ ይላል፤ [25]ሲመለስም ቤቱ ተጠራርጎና ተስተካክሎ ያገኘዋል:: [26]ከዚያም በኋላ ሄዶ ሌሎች ከእርሱ የከፉ ሰባት አጋንንት ይዞ ይመጣል፤ ገብተውበትም በዚያ ይኖራሉ፤ ለዚያ ሰው ከመጀመሪያው ይልቅ የኋለኛው ሁኔታ የከፋ ይሆንበታል::

[27]ኢየሱስ ይህን እየተናገረ እያለ፣ ከሕዝቡ መካከል አንዲት ሴት ድምፅዋን ከፍ አድርጋ፣ “የተሸከመችህ ማሕፀንና የጠባሃቸው ጡቶች ብፁዓን ናቸው” አለችው::

[28]እርሱ ግን፣ “ብፁዓንስ የእግዚአብሔርን ቃል ሰምተው የሚታዘዙት ናቸው” አለ::

11፥17 ማቴ9፥4
11፥18 ማቴ4፥10
11፥20 ዘፀ8፥19፤ ማቴ3፥2
11፥23 ማቴ12፥30፤ ማር9፥40፤ሉቃ9፥50
11፥26 2ጴጥ2፥20
11፥27 ሉቃ23፥29
11፥28 ምሳ8፥32፤ ሉቃ6፥47፤8፥21፤ዮሐ 14፥21፤ዕብ 4፥12
11፥29 ቍ16፤ ዮና1፥17፤ ማቴ12፥38፤16፥4
11፥31 1ነገ10፥1፤ 2ዜና9፥1
11፥32 ዮና3፥5
11፥33 ማቴ5፥15

## የዮናስ ምልክትነት

11፥29-32 ተጓ ምብ – ማቴ 12፥39-42

[29]ብዙ ሕዝብ እየተሰበሰበ በሄደ ጊዜ ኢየሱስ እንዲህ ይል ጀመር፤ “ይህ ትውልድ ክፉ ነው፤ ታምራዊ ምልክት ይፈልጋል፤ ነገር ግን ከዮናስ ምልክት በስተቀር ሌላ አይሰጠውም:: [30]ምክንያቱም ዮናስ ለነነዌ ሰዎች ምልክት እንደ ሆናቸው የሰው ልጅም ለዚህ ትውልድ ምልክት ይሆናል:: [31]የደቡብ ንግሥት በፍርድ ጊዜ ከዚህ ትውልድ ጋር ተነሥታ ትፈርድባቸዋለች፤ እርሷ የሰሎሞንን ጥበብ ለመስማት ከምድር ዳርቻ መጥታለችና፤ እነሆ፣ ከሰሎሞን የሚበልጥ እዚህ አለ:: [32]የነነዌ ሰዎችም በፍርድ ጊዜ ከዚህ ትውልድ ጋር ተነሥተው ይፈርዱበታል፤ እነርሱ የዮናስን ስብከት ሰምተው ንስሓ ገብተዋልና፤ እነሆ፣ ከዮናስ የሚበልጥ እዚህ አለ::

## የሰውነት መብራት

11፥34:35 ተጓ ምብ - ማቴ 6፥22:23

[33]“መብራት አብርቶ በስውር ቦታ ወይም ከእንቅብ በታች የሚያስቀምጥ ማንም የለም፤ ይልቁን የሚገቡ ሰዎች ብርሃኑን እንዲያዩ በመቅረዝ ላይ ያስቀምጠዋል:: [34]የሰውነትህ ብርሃን ዐይንህ ናት፤ ዐይንህ ጤናማ ስትሆን መላ ሰውነትህ ብሩህ ይሆናል፤ ዐይንህ ታማሚ ከሆነች ግን መላ ሰውነትህ የጨለመ

[u]24 ወይም *ክፉ*

11፥17 *እርስ በርሱ የሚከፋፈል መንግሥት፤* በማንኛውም ረገድ ለሚቃወመው ለኢየሱስ ሰይጣን ሥልጣን የሚሰጠው ከሆነ፣ ራሱን የሚያጠፋውን ኀይል መደገፍ ይሆንበታል::

11፥19 *ልጆቻችሁ በማን...?* የፈሪሳውያን ተከታዮች (ማቴ 12፥24 ይመ) አጋንንትን ስለ ማውጣታቸው ኢየሱስ አልተናገረም (የቍ24 ማብ ይመ) ፤ ይሁን እንጂ እነርሱ በእግዚአብሔር ኀይል አጋንንትን እናስወጣለን ይላሉ፤ ኢየሱስም አጋንንትን በእግዚአብሔር ኀይል እንዳስወጣ ተናገረ፤ ስለዚህ “በሰይጣን ኀይል ርኩስ መንፈስን አስወጥተሃል” ብለው ኢየሱስን ስለከሰሱ፣ በተዘዋዋሪ መንገድ ተከታዮቻቸውንም ተቃውመዋል ማለት ነው:: *ፈራጆች ይሆኑባችኋል፤* በእነርሱ ላይ ክስ ስላቀረባችሁ፣ እነርሱ ራሳቸው ይፈርዱባችኋል::

11፥20 *የእግዚአብሔር መንግሥት... እንደ መጣች፤* ይኸውም ንጉሡ የሆነው ኢየሱስ ስለመጣና (የ 4፥43 ማብ ይመ) የክፉ መንፈስ ኀይል ስለ ተሰበረ ነው::

11፥22 *ይበልጥ ብርቱ የሆነ ሰው... ካጠቃውና፤* ኢየሱስ፣ ከብዔል ዜቡል የበረታ ነው፤ አጋንንትን ከሰዎች በማስወጣት፣ ሰይጣንን እንዳሸነፈና ሥልጣኑንም እንደቀማው አሳየ፤ በዚህ ምክንያት፣ ኢየሱስ አጋንንትን ከሰዎች ውስጥ ያስወጣ በሰይጣን ኀይል ነው ማለቱ ሞኝነት ነው::

11፥23 *ከእኔ ጋር ያልሆነ ይቃወመኛል፤* ገለልተኛ መሆን የሚቻልበት አማራጭ የለም:: ደቀ መዛሙርት በ9፥50 ላይ “ከእኛ ወገን አይደለም” ያሉት ሠራተኛ እንኳ፣ በኢየሱስ ስም ታምር የሚያደርግ አማኝ ነበር (የማር 9፥38 ማብ ይመ)፤ ኢየሱስም ይህን ሰው አልነቀፈውም::

11፥24 *ርኩስ መንፈስ ... ሲወጣ፤* እዚህ ላይ ኢየሱስ ይህን የተናገረው አጋንንትን እናስወጣለን ስለሚሉት (ከቍ19 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ነገር ግን የእግዚአብሔርን መንግሥት ለመቀበል ፈቃደኞች ስላልሆኑት አይሁዳውያን ሳይሆን አይቀርም፤ የእርሱ አጋንንትን ማስወጣትም ዘላቂ መፍትሔ አልነበረውም:: ኢየሱስ በዚያን ዘመን ስለ ነበረው የአይሁድ ሕዝብ የተናገረውን ተመሳሳይ ሐሳብ በማቴ 12፥43-45 ይመ::

11፥25 *ቤቱ ተጠራርጎ ... ያገኘዋል፤* ቦታው የጸዳ ቢሆንም፣ በሌላ አልተተካም፤ ከክፉ መንፈስ ነጻ ወጥቶ የእግዚአብሔር ማደሪያ ባልሆነ ሕይወት፣ ክፉ መንፈስ ተመልሶ ይገባበት ዘንድ በሩ ክፍት ነው::

11፥29 *ታምራዊ ምልክት ይፈልጋል፤* አይሁዳውያን ብዙ ጊዜ ታምራዊ ምልክት ያዩ ዘንድ ቢጠይቁም (ቍ16፤ ማቴ 12፥38፤ ማር 8፥11)፣ የጠየቁበት ዐላማ ትክክል ስላልነበረ ኢየሱስ አልተቀበላቸውም::

11፥30 *ዮናስ...ምልክት እንደ ሆናቸው፤* ዮናስ በዓሣ ነባሪ ሆድ ውስጥ ሦስት ቀን እንደ ነበረ ሁሉ፣ ኢየሱስም ከትንሣኤው በፊት ሦስት ቀን በመቃብር ውስጥ ነበር (የማቴ 12፥40 ማብ ይመ)::

11፥31-32 *ከሰሎሞን የሚበልጥ ... ከዮናስ የሚበልጥ፤* ኢየሱስ ትምህርቱን ያቀረበው ከትንሽ ጉዳይ በመነሣት፣ ትልቅ ወደ ሆነው በማምራት ነው፤ የሳባ ንግሥት፣ የሰሎሞንን ጥበብ ከተቀበለችና የነነዌ ሰዎችም የዮናስን ስብከት ከተቀበሉ፣ በጌታ ዘመን የነበሩት ሰዎች፣ ከሰሎሞንና ከዮናስ እጅግ የሚበልጠውን የኢየሱስን ትምህርት ሊቀበሉ ይገባቸው ነበር::

11፥31 *የደቡብ ንግሥት፤* የሳባ ንግሥት ማለት ነው (1ነገ 10፥1-10 እና ማብ ይመ)::

11፥33 *ከእንቅብ፤* ከቍና ከፍ የሚልና 9 ኪሎ ግራም ያህል እህል የሚይዝ ነው:: *ብርሃኑን እንዲያዩ፤* የመብራት ጥቅም በአጠገቡ ላሉት ሰዎች ብርሃን መስጠት ነው (ቍ36 ይመ)፤ ኢየሱስም ለሁሉም የወንጌልን ብርሃን ሰጠ፤ አይሁዳውያን ግን አስደናቂና ስሜት ማራኪ የሆኑ ምልክቶችን ለማየት ፈለጉ:: የአይሁድ የማስተዋል ችሎታ የተዛባ ሆኖ እንጂ፣ የዓለም ብርሃን የሆነው (ዮሐ 8፥12) ኢየሱስ ክርስቶስ አጠገባቸው ነበር::

11፥34 *ዐይንህ ጤናማ ስትሆን፤* ምልክትን የሚፈልጉ አይሁዳውያን፣ የሚያስፈልጋቸው ተጨማሪ ብርሃን ሳይሆን፣ ብርሃንን የሚቀበል ጤናማ ዐይን ነው::

ይሆናል:: [35]ስለዚህ በውስጥህ ያለው ብርሃን ጨለማ እንዳይሆን ተጠንቀቅ:: [36]እንግዲህ ሰውነትህ ሁሉ ብሩህ ከሆነና የጨለመ የሰውነት ክፍል ከሌለበት፣ የሰውነትህ ሁለንተና መብራት በወገግታው ያበራልህ ያህል ይደምቃል::"

## ስድስት ዐይነት ወዮታ

[37]ኢየሱስ ንግግሩን እንደ ጨረሰ፣ አንድ ፈሪሳዊ ከእርሱ ጋር ምግብ እንዲበላ ጋበዘው፤ እርሱም አብሮት ገብቶ በማእድ ተቀመጠ:: [38]ፈሪሳዊውም ኢየሱስ ከምግብ በፊት እጁን እንዳልታጠበ ባየ ጊዜ ተደነቀ::

[39]ጌታም እንዲህ አለው፤ "እሁን እናንተ ፈሪሳውያን የጽዋውንና የወጭቱን ውጫዊ ክፍል ታጸዳላችሁ፤ ውስጣችሁ ግን በስስትና በክፋት የተሞላ ነው:: [40]እናንተ ሞኞች፤ የውጪውን የፈጠረ የውስጡንም አልፈጠረምን? [41]ነገር ግን በውስጥ ያለውን ምጽዋት[a] አድርጋችሁ ስጡ፤ በዚህ ጊዜ ሁሉም ንጹሕ ይሆንላችኋል::

[42]"እናንተ ፈሪሳውያን ግን ወዮላችሁ፤ ከአዝሙድና ከጤና አዳም እንዲሁም ከአትክልት ሁሉ ዐሥራት ታወጣላችሁ፤ ሆኖም ፍትሕንና እግዚአብሔርን መውደድ ቸል ትላላችሁ፤ ነገር ግን ያንን ሳትተዉ ይኸኛውን ማድረግ በተገባችሁ ነበር::

[43]"እናንተ ፈሪሳውያን ወዮላችሁ በምኵራብ የክብር መቀመጫ፣ በገበያ መካከልም እጅ መነሣትን ትወዳላችሁና::

[44]"ሰዎች ሳያውቁ በላዩ የሚሄዱበትን የተሰወረ መቃብር ስለምትመስሉ፣ ወዮላችሁ"::

[45]ከሕግ ዐዋቂዎች አንዱ መልሶ "መምህር ሆይ፤ እንዲህ ስትናገር እኮ እኛንም መስደብህ ነው" ሲል መለሰለት::

[46]ኢየሱስም እንዲህ አለ፤ "እናንተ ሕግ ዐዋቂዎችም ደግሞ ወዮላችሁ፤ ሰዎች ሊሸከሙ የማይችሉትን ከባድ ሸክም ታሸክማላችሁ፤ እናንተ ራሳችሁ ግን በጣታችሁ እንኳ አትነኩትም::

[47]"አባቶቻችሁ የገደሏቸውን የነቢያትን መቃብር ስለምታበጃጁ፣ ወዮላችሁ፤ [48]እንግዲህ የአባቶቻችሁን ሥራ የምታጸኑ ምስክሮች ናችሁ፤ እነርሱ ነቢያትን ገደሉ፣ እናንተም መቃብራቸውን ታበጃጃላችሁ:: [49]ስለ ዚህም የእግዚአብሔር ጥበብ እንዲህ አለች፤ 'ነቢያትንና ሐዋርያትን እልክላቸዋለሁ፤ እነርሱ አንዳንዶቹን ይገድላሉ፤ ሌሎችንም ያሳድዳሉ::' [50]ስለዚህ ይህ ትውልድ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ስለፈሰሰው፣ ስለ ነቢያት ሁሉ ደም ተጠያቂ ነው፤ [51]ከአቤል ደም ጀምሮ፣ በመሠዊያውና በቤተ መቅደሱ መካከል እስከ ፈሰሰው እስከ ዘካርያስ ደም ድረስ ይፈለግበታል፤ አዎን፣ እላችኋለሁ፤ ይህ ትውልድ ለዚህ ተጠያቂ ነው::

[52]"እናንተ ሕግ ዐዋቂዎች ወዮላችሁ፤ የዕውቀትን መክፈቻ ነጥቃችሁ ወስዳችኋልና፤ እናንተ ራሳችሁ አልገባችሁበትም፤ የሚገቡትንም ከልክላችኋል::"

[53]ኢየሱስ ከዚያ ከወጣ በኋላ፣ ጸሐፍትና ፈሪሳውያን ክፉኛ ይቃወሙትና በጥያቄም ያዋክቡት ጀመር፤ [54]ከአፉ በሚወጣውም ቃል ሊያጠምዱት ያደቡ ነበር::

## የማስጠንቀቂያና የማበረታቻ ቃላት

12፥2-9 ተጓ ምብ-ማቴ 10፥26-33

**12** በዚያን ጊዜ፣ በብዙ ሺህ የሚቈጠር ሕዝብ እርስ በርስ እስኪረጋገጥ ድረስ ተሰብስቦ ሳለ፣ ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ ይል ጀመር፤ "ከፈሪሳውያን እርሾ ተጠንቀቁ፤ ይህም ግብዝነት ነው::

[a]41 ወይም *ያላችሁን*

11፥37 ሉቃ7፥36፤ 14፥1
11፥38 ማር7፥3፡4
11፥39 ማቴ23፥25፡26፤ማር7፥20-23፤ ሉቃ7፥13
11፥40 ሉቃ12፥20፤ 1ቆሮ15፥36
11፥41 ሉቃ12፥33፤ሐሥ10፥15
11፥42 ዘሌ6፥5፤ ሚክ6፥8፤ማቴ23፥23፤ ሉቃ18፥12
11፥43 ማቴ23፥6፤ ሉቃ14፥7፤20፥46
11፥44 ማቴ23፥27
11፥45 ማቴ22፥35
11፥46 ማቴ23፥4
11፥48 ማቴ23፥29-32፤ሐሥ7፥51-53
11፥49 ማቴ23፥24፤ 1ቆሮ1፥24፡30፤ቈላ2፥3
11፥52 ማቴ23፥13
11፥54 ማቴ12፥10
12፥1 ማቴ16፥6፡ 11፡12

11፥38 *በፊት እጁን እንዳልታጠበ፤* በሕግ የታዘዘ ሳይሆን፣ በፈሪሳውያን ልማድ የተጨመረና በተለይም ለመንጻት ሥርዐት ሲባል የሚደረግ ነው (ማር 7፥3፤ ከማቴ 15፥9 ጋር ያነጻጽሩ)::

11፥39 *ውጫዊ ክፍል ታጸዳላችሁ፤* በሥርዐቱ መሠረት ለመንጻት የሚደረገውን መተጣጠብ ያመለክታል:: *በስስትና በክፋት፤* እነዚህ ፈሪሳውያን ይጨነቁ የነበሩት መልካም ምግባርን ለመከተል ሳይሆን፣ ወግና ሥርዐትን ለመጠበቅ ነበር (ከማር 7፥20-23 ጋር ያነጻጽሩ)::

11፥40 *የውስጡንም አልፈጠረምን?* የሰው የውስጥ ሰውነት (የልብ ንጽሕናና ጽድቅ)፣ ውጫዊ ከሆነው በሥርዐቱ መሠረት (ከመንጻት) ይልቅ እጅግ አስፈላጊ ነው::

11፥41 *በውስጥ ያለውን፤* በቍ 39 ላይ ከሰፈረው የአነጋገር ዘይቤ ጋር ይመሳሰላል:: *ሁሉም ንጹሕ ይሆንላችኋል፤* ስጦታን ከልብ መስጠት መንፈሳዊ ጠቀሜታ አለው፤ ስለዚህም ማንም በቅንነት ለድኻ ቢሰጥ፣ ልቡ በስስትና በክፋት ወጥመድ ውስጥ አይገባም (ቍ 39)::

11፥44 *የተሰወረ መቃብር፤* አንድ ሰው በድንገት መቃብርን በመንካት እንዳይረክስ፣ አይሁዳውያን መቃብራቸውን ኖራ ይቀቡ ነበር (ከዘኍ 19፥16፤ ማቴ 23፥27 ጋር ያነጻጽሩ):: መቃብርን መንካት በሥርዐቱ መሠረት ርኩስ እንደሚያደርግ ሁሉ፣ ከፈሪሳውያን ጋር ኅብረት ማድረግም በሥነ ምግባር ረገድ ርኩስ ያደርጋል::

11፥45 *ሕግ ዐዋቂዎች፤* የ7፥30 ማብ ይመ::

11፥46 *ሰዎች... ሸክም ታሸክማላችሁ፤* ሙሴ በሰጣቸው እውነተኛ ሕግ ላይ ሕግጋትንና ደንቦችን በመጨመርና (የማቴ 15፥2 ማብ ይመ) ሌሎች ሰዎች ሕጉን መጠበቅ የሚችሉበትን መንገድ ባለማሳየት፣ ራሳቸው ከሕግ እስራት የሚያመልጡበትን መንገድ ያመቻቹ ነበር (ማቴ 23፥4)::

11፥47 *የነቢያትን መቃብር፤* አይሁዳውያን ለነቢያት መታሰቢያ ሐውልትን ስለሚሰሩና የተሰራውንም ስለሚያድሱ፣ ነቢያትን የሚያከብሩ ይመስላሉ፤ ሆኖም ግን ነቢያት የመሰከሩለትን ክርስቶስን በልባቸው ይክዳሉ:: ቀደምት አባቶቻቸው እንዳደረጉት ሁሉ፣ እነርሱም ነቢያት ያስተማሩትን ትምህርት አይቀበሉም::

11፥49 *የእግዚአብሔር ጥበብ እንዲህ አለች፤* ከብሉይ ኪዳን፣ ወይም ከሌላ ዕውቅ መጽሐፍ የተገኘ ጥቅስ አይደለም:: እግዚአብሔር አብ፣ በኢየሱስ በኩል መናገሩን ወይም ነቢያትንና ሐዋርያትን እንደማይቀበሏቸው ቢያውቅም፣ እግዚአብሔር እነዚህኑ ለመላክ መወሰኑን የሚያመለክት፣ በጥቅስ መልክ የተገለጸ ሐሳብ ነው::

11፥51 *ከአቤል ደም... እስከ ዘካርያስ፤* የማቴ 23፥35 ማብ ይመ::

11፥52 *የዕውቀትን መክፈቻ፤* እነዚህ ሕግን ሊያስተምሩ የሚገባቸውን መምህራን፣ በተሳሳተ ትርጓሜና መስመር በለቀቀ ትምህርተ መለኮታቸው የገዛ አእምሮአቸውን አጨለሙ፤ ስለዚህም ራሳቸውን ዐሳውረው ሕዝቡ የድነትን መንገድ እንዳያውቅ አደረጉ፤ ወይም "የእግዚአብሔርን መንግሥት በሰዎች ላይ የምትዘጉ ናችሁ" ብሎ ማቴዎስ እንደጻፈው ሆነባቸው (ማቴ 23፥13)::

11፥54 *ሊያጠምዱት ያደቡ ነበር፤* የሃይማኖት አለቆች፣ ኢየሱስን ለማጥመድ ቍርጥ ሐሳብ አድርገው እንደ ነበር በሉቃስ ወንጌል ውስጥ በግልጽ ተጠቅሶአል (6፥11፤19፥47-48፤ 20፥19-20፤22፥2)::

12፥1 *ከፈሪሳውያን እርሾ፤* የማር 8፥15 ማብ ይመ::

[2]የማይገለጥ የተሸፈነ፣ የማይታወቅ የተሰወረ ምንም የለም። [3]ስለዚህ በጨለማ ያወራችሁት ሁሉ በብርሃን ይሰማል፤ በእልፍኝም ውስጥ በጆሮ ያንሾካሾካችሁት በሰገነት በይፋ ይነገራል።

[4]"ወዳጆቼ ሆይ፤ እላችኋለሁ ሥጋን የሚገድሉትን፣ ከዚያ ወዲያ ግን ምንም ማድረግ የማይችሉትን አትፍሩ። [5]ነገር ግን መፍራት የሚገባችሁን አሳያችኋለሁ፤ ከገደለ በኋላ ወደ ገሃነም ለመጣል ሥልጣን ያለውን እርሱን ፍሩት፤ አዎን፤ እርሱን ፍሩት እላችኋለሁ። [6]አምስት ድንቢጦች በዐሥር ሳንቲም[ሐ] ይሸጡ የለምን? ይሁን እንጂ ከእነርሱ አንዷ እንኳ በእግዚአብሔር ዘንድ አትዘነጋም። [7]የእናንተ የራሳችሁ ጠጕር ሁሉ እንኳ የተቈጠረ ነው፤ እንግዲህ አትፍሩ፤ ከብዙ ድንቢጦች የበለጠ ዋጋ አላችሁ።

[8]"እላችኋለሁ፤ በሰው ፊት ለሚመሰክርልኝ ሁሉ የሰው ልጅ ደግሞ በእግዚአብሔር መላእክት ፊት ይመሰክርለታል። [9]በሰው ፊት የሚክደኝም በእግዚአብሔር መላእክት ፊት ይካዳል። [10]በሰው ልጅ ላይ የማቃለል ቃል የሚሰነዝር ሁሉ ይሰረይለታል፤ መንፈስ ቅዱስን የሚሳደብ ግን አይሰረይለትም።

[11]"ሰዎች ይዘው ወደ ምኵራብ፣ ወደ ገዦዎችና ወደ ባለ ሥልጣናት ባቀረቧችሁ ጊዜ፣ እንዴት ወይም ምን እንደምትመልሱ አትጨነቁ፤ [12]በዚያ ሰዓት መንፈስ ቅዱስ መናገር የሚገባችሁን ያስተምራችኋልና።"

## የሀብታሙ ሰው ሞኝነት

[13]ከሕዝቡም መካከል አንድ ሰው፣ "መምህር ሆይ፤ ወንድሜ ውርስ እንዲያካፍለኝ ንገረው" አለው።

[14]ኢየሱስም፣ "አንተ ሰው፤ በእናንተ ላይ ፈራጅ ወይም ዳኛ ያደረገኝ ማነው?" አለው። [15]ደግሞም፣ "የሰው ሕይወቱ በሀብቱ ብዛት የተመሠረተ ስላልሆነ፣ ተጠንቀቁ፤ ከስግብግብነትም ሁሉ ራሳችሁንም ጠብቁ" አላቸው።

[16]ቀጥሎም እንዲህ ሲል ምሳሌ ነገራቸው፤ "ዕርሻው እጅግ ፍሬያማ የሆነችለት አንድ ሀብታም ነበረ፤

[17]ይህም ሰው፣ ምርቴን የማከማችበት ስፍራ ስለሌለኝ ምን ላድርግ? ብሎ በልቡ አሰበ።

[18]"እንዲህም አለ፤ እንደዚህ አደርጋለሁ፤ ያሉኝን ጐተራዎች አፈርስና ሌሎች ሰፋ ያሉ ጐተራዎች እሠራለሁ፤ በዚያም ምርቴንና ንብረቴንም ሁሉ አከማቻለሁ፤ [19]ነፍሴንም፣ "ነፍሴ ሆይ፤ ለብዙ ዘመን የሚበቃሽ ሀብት አከማችቼልሻለሁ፤ እንግዲህ ዕረፊ፤ ብዪ፤ ጠጪ፤ ደስም ይበልሽ'' እላታለሁ።

[20]"እግዚአብሔር ግን፣ አንተ ሞኝ፤ ነፍስህን በዚህች ሌሊት ከአንተ ሊወስዱ ይፈልጓታል፤ እንግዲህ፣ ለራስህ ያከማቸኸው ለማን ይሆናል? አለው።

[21]"ስለዚህ ለራሱ ሀብት የሚያከማች፣ ዳሩ ግን በእግዚአብሔር ዘንድ ሀብታም ያልሆነ ሰው መጨረሻው ይኸው ነው።"

## አትጨነቁ

12፥23-31 ተጓ ምብ – ማቴ 6፥25-33

[22]ከዚያም ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አለ፤ "ስለዚህ እላችኋለሁ፣ ስለ ሕይወታችሁ ምን እንደምትበሉ፣ ወይም ስለ ሰውነታችሁ ምን እንደምትለብሱ አትጨነቁ፤ [23]ሕይወት ከምግብ፣ ሰውነትም ከልብስ ይበልጣልና። [24]ቁራዎችን ተመልከቱ፤ አይዘሩም፤ አያጭዱም፤ ማከማቻ ወይም ጐተራ የላቸውም፤ እግዚአብሔር ግን ይመግባቸዋል። እናንተማ ከወፎች እጅግ ትበልጡ የለምን? [25]ለመሆኑ ከእናንተ ተጨንቆ በዕድሜው ላይ አንዲት ደቂቃ መጨመር የሚችል ማነው?[ሠ] [26]እንግዲህ ቀላሉን ነገር እንኳ ማድረግ የማትችሉ ከሆነ፣ ስለ ሌላው ነገር ለምን ትጨነቃላችሁ?

[27]"እስቲ አበቦች እንዴት እንደሚያድጉ ተመልከቱ፤ አይለፉም፤ አይፈትሉም፤ ነገር ግን እላችኋለሁ፤ ሰሎሞን እንኳ በዚያ ሁሉ

[ሐ]6 ግሪኩ ሁለት ሊሳሪያ ይላል
[ሠ]25 ወይም በቍመት ላይ አንድ ክንድ

12፥2 ማር4፥22
12፥4 ዮሐ15፥14፡15
12፥5 ዕብ10፥31
12፥7 ማቴ10፥30፤ 12፥12
12፥8 ሉቃ15፥10
12፥10 ማቴ8፥20፤ 12፥31፡32፤ 1ዮሐ5፥16
12፥11 ማቴ10፥ 17፡19፤ ሉቃ21፥12፡14
12፥12 ዘፀ4፥12፤ ማቴ10፥20፤13፥11፤ ሉቃ21፥15
12፥15 ኢዮ20፥20፤ 31፥24፤መዝ62፥10
12፥20 ኢዮ27፥8፤ መዝ39፥6፤49፥10፤ ኤር17፥11፤ ሉቃ11፥40
12፥21 ቍ33
12፥24 ኢዮ38፥41፤ መዝ147፥9
12፥27 1ነገ10፥4-7

12፥2 *የማይገለጥ የተሸፈነ...የለም፤* በዚህ ዐውደ ምንባብ መሠረት በግብዝነት የተደበቀ ሁሉ ሳይገለጥ አይቀርም ማለት ነው።

12፥3 *በእልፍኝም ውስጥ፤* ማንም ሰው ሰርስሮ እንዳይገባ ሲባል፣ እንዲህ ዐይነቱ ቤት በሌሎች ክፍሎች መካከል ይሠራ ነበር።

12፥4 *ከዚያ ወዲያ ግን ምንም ማድረግ የማይችሉትን፤* በስደት ጊዜ የሚጠቅም፣ የሚያበረታታ ቃል ነው (ማቴ 10፥28 ይመ)።

12፥5 *ወደ ገሃነም ለመጣል ሥልጣን ያለውን፤* ይህ ዐይነት ሥልጣን ያለው፣ እግዚአብሔር ብቻ ነው። 'ገሃነም' የሚለው ቃል ከግሪኩ የተወሰደ ሲሆን (የማቴ 5፥22 ማብ ይመ)፣ ሙታን እስከ ፍርድ ቀን ድረስ የሚጠበቁበት ቦታ ከሆነ "ከሲኦል" ጋር አንድ አይደለም፤ በአዲስ ኪዳን ውስጥ "ገሃነም" የሚለው ቃል ተጠቅሶ የሚገኘው በማቴዎስ፣ በማርቆስ፣ በያዕቆብ 3፥6 እና በዚህ ወንጌል ውስጥ ብቻ ነው። *እርሱን ፍሩት፤* ሥልጣኑን አክብሩ፤ በግርማው ፊት በፍርሀት ቁሙ፤ በእርሱም ታመኑ ማለት ነው። ቍ6-7 ለምን በእግዚአብሔር መታመን እንደሚያስፈልግ ያስረዳል።

12፥6 *አምስት ድንቢጦች በዐሥር ሳንቲም፤* ለምግብነት በርካሽ ዋጋ ለሚሸጡት ድንቢጦች እንኳ ሳይቀር እግዚአብሔር ያስባል።

12፥8 *ለሚመሰክርልኝ፤* ኢየሱስ፣ መሲሕና የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑን አንድ ሰው ሲመሰክር (ማቴ16፥16፤ 1ዮሐ2፥22)፣ ኢየሱስም ያ ሰው ታማኝ የእርሱ ተከታይ መሆኑን ይመሰክርለታል (ከማቴ 7፥21 ጋር ያነጻጽሩ)።

12፥9 *ይካዳል፤* 9፥26፤ 2ጢሞ 2፥12 ይመ፤ ከማቴ7፥21፤ 25፥41-46 ጋር ያነጻጽሩ። ጴጥሮስ ኢየሱስን እንደሚክደው የተነገረውም በዚሁ ቃል ነው ("ትክደኛለህ" ሉቃ 22፥34፡61)።

12፥10 *መንፈስ ቅዱስን የሚሳደብ፤* የማቴ 12፥31 ማብ ይመ፤ ከማር 3፥28-29 ጋር ያነጻጽሩ።

12፥13 *ውርስ እንዲያካፍለኝ፤* የበኵር ልጅ የሆነ ሁሉ፣ የታናሹን ድርሻ ዕጥፍ ሊወርስ እንደሚገባው በዘዳ 21፥17 ላይ ተጽፎአል። የውርስ ክርክር ሲነሣ ብያኔ የሚሰጡት፣ የአይሁድ ሃይማኖት መምህራን ናቸው፤ ሰውዬው ለኢየሱስ ያቀረበው ይህ ጥያቄ፣ ራስ ወዳድነቱን ብቻ ሳይሆን ቍሳዊ በሆነ ነገር ላይ ልቡን የጣለ መሆኑን ያመለክታል፤ ጌታ ኢየሱስ ሲያስተምርም፣ ይህ ሰው ከልብ ያዳመጠ አይመስልም (ከቍ1-11 ጋር ያነጻጽሩ)። ኢየሱስ፣ የሰውየውን ጥያቄ የመለሰው ስስት የሚያስከትለውን ጠንቅ በተምሳሌት በማስተማር ነው።

12፥16 *ምሳሌ፤* የ8፥4 ማብ ይመ።

12፥20 *ሞኝ፤* ጠንከር ያለ መልእክት ያዘለ ቃል ነው (11፥40፤ ኤፌ 5፥17)።

ክብሩ ከእነርሱ እንደ አንዷ አልለበሰም። [28]እንግዲህ ስግዚስብሔር ዛሬ ታይቶ ነገ ወደ እሳት የሚጣለውን የሜዳ ሣር እንዲህ የሚያለብስ ከሆነ፣ እናንተ እምነት የጐደላችሁ፣ እናንተንማ እንዴት አብልጦ አያለብሳችሁም? [29]ስለዚህ ምን እንደምትበሉና ምን እንደምትጠጡ በመሻት ልባችሁ አይጨነቅ፤ [30]ይህንማ በዓለም ያለ ሕዝብ ሁሉ ይፈልጋል፤ አባታችሁ እኮ ይህ ሁሉ እንደሚያስፈልጋችሁ ያውቃል። [31]ይልቁንስ የስግዚስብሔርን *መንግሥት ፈልጉ*፤ ይህም ሁሉ በተጨማሪ ይሰጣችኋል።

[32]"እናንተ አነስተኛ *መንጋ* የሆናችሁ *መንግሥትን* ሊሰጣችሁ የአባታችሁ *መል*ካም *ፈቃድ* ነውና አትፍሩ፤ [33]ያላችሁን ሽጡና ለድኾች ስጡ፤ ሌባ በማይሰርቅበት፣ ብል በማይበላበት፣ በማያረጅ ከረጢት የማያልቅ ንብረት በሰማይ አከማቹ፤ [34]ልባችሁ፣ ንብረታችሁ ባለበት ቦታ ይሆናልና።

## ነቅቶ መጠበቅ

12፥35፡36 ተጓ ምብ -ማቴ 251-13፤ ማር 13፥33-37
12፥39፡40፤ 42-46 ተጓ ምብ – ማቴ 24፥ 43-51

[35]"በአጭር ታጥቃችሁ ተዘጋጁ፤ መብራታችሁም የበራ ይሁን፤ [36]ጌታቸው ከሰርግ ግብዣ እስኪመለስ እንደሚጠባበቁና መጥቶም በር ሲያንኳኳ ወዲያው ለመክፈት ዝግጁ የሆኑ ሰዎችም ምሰሉ። [37]ጌታቸው በሚመጣበት ጊዜ ነቅተው የሚያገኛቸው አገልጋዮች ብፁዓን ናቸው፤ እውነት እላችኋለሁ፤ ጌታቸውም በአጭር ይታጠቃል፤ በማእድ ያስቀምጣቸዋል፤ ቀርቦም ያስተናግዳቸዋል። [38]ከሌሊቱ በሁለተኛውም ሆነ በሦስተኛው ክፍል መጥቶ እንደዚያው ነቅተው ቢያገኛቸው፣ እነዚያ አገልጋዮች ብፁዓን ናቸው። [39]ይህን ግን ዕወቁ፤ ሌባ በምን ሰዓት እንደሚመጣ የቤቱ ባለቤት ቢያውቅ ኖሮ፣ ቤቱ ሲቈፈር ዝም ብሎ ባላየ ነበር። [40]እናንተም ተዘጋጅታችሁ ጠብቁ፤ የሰው ልጅ ባላሰባችሁት ሰዓት ይመጣልና።"

[41]ጴጥሮስም፣ "ጌታ ሆይ፤ ይህን ምሳሌ የምትናገረው ለእኛ ብቻ ነው ወይስ ለሁሉም ጭምር ነው?" አለው።

[42]ጌታም እንዲህ ሲል መለሰ፤ "እንግዲህ፣ ምግባቸውን በተገቢው ጊዜ እንዲሰጣቸው ጌታው በቤተ ሰዎቹ ላይ የሚሾመው ታማኝና ብልህ መጋቢ ማነው? [43]ጌታው ሲመለስ እንዲህ ሲያደርግ የሚያገኘው አገልጋይ እርሱ ብፁዕ ነው። [44]እውነት እላችኋለሁ፤ ባለው ንብረት ሁሉ ላይ ይሾመዋል። [45]ዳሩ ግን ያ አገልጋይ፣ ጌታዬ ቶሎ አይመጣም፤ ይዘገያል፤ ብሎ ቢያስብና ወንድና ሴት አገልጋዮችን ቢደበድብ፣ ደግሞም እንዳሻው መብላት፣ መጠጣትና መስከር ቢጀምር፣ [46]የዚያ አገልጋይ ጌታ ባላሰበው ቀንና ባልጠረጠረው ሰዓት ይመጣበታል፤ ስለዚህ ይቈራርጠዋል፤ ዕድል ፈንታውንም ከማያምኑ ጋር ያደርጋል።

[47]"የጌታውን ፍላጎት እያወቀ የማይዘጋጅና ፈቃዱን የማያደርግ አገልጋይ እርሱ ከፉኛ ይገረፋል፤ [48]ነገር ግን ይህን ሳያውቅ ቀርቶ መገረፍ የሚገባውን ያህል ያደረገ አገልጋይ በጥቂቱ ይገረፋል። ብዙ ከተሰጠው ሁሉ ብዙ ይፈለግበታል፤ ብዙ ዐደራም ከተቀበለም ብዙ ይጠበቅበታል።

## ሰላም ሳይሆን መለያየት

12፥51-53 ተጓ ምብ – ማቴ 10፥34-36

[49]"እኔ የመጣሁት በምድር ላይ እሳት ለመለኰስ ነው፤ አሁኑኑ ቢቀጣጠል ምንኛ ደስ ባለኝ! [50]ነገር ግን የምጠመቀው ጥምቀት አለኝ፤ እስኪፈጸምም ድረስ እንዴት ተጨንቄአለሁ? [51]በምድር ላይ ሰላምን ለማምጣት የመጣሁ ይመስላችኋል? አይደለም፤ እላችኋለሁ፤ እኔ የመጣሁት ለመለያየት ነው። [52]ከአሁን ጀምሮ እርስ በርስ የተለያዩ በአንድ ቤተ ሰብ ውስጥ አምስት ሰዎች ይኖራሉ፤ ሁለቱ በሦስቱ ላይ፣ ሦስቱም በሁለቱ ላይ ተነሥተው ይለያያሉ፤ [53]አባት በወንድ ልጁ ላይ፣ ወንድ ልጅም በአባቱ ላይ፣ እናት በሴት ልጇ ላይ፣ ሴት ልጅም በእናቷ ላይ፣

12፥28 ማቴ6፥30
12፥30 ማቴ6፥8፤ ሉቃ6፥36
12፥31 ማቴ3፥2፤ 19፥29
12፥32 ማቴ14፥27፤ 25፥34
12፥33 ማቴ6፥20፤ ሐሥ2፥45፤ያዕ5፥2
12፥34 ማቴ6፥21
12፥37 ማቴ20፥28፤ 24፥42፡46፤25፥13
12፥39 ማቴ6፥19፤1ተሰ5፥2፤ 2ጴጥ3፥10፤ራእ3፥3፤ 16፥15
12፥40 ማር13፥33፤ ሉቃ21፥36
12፥42 ሉቃ7፥13
12፥46 ቍ40
12፥47 ዘዳ25፥2
12፥48 ዘሌ5፥17፤ ዘኍ15፥27-30
12፥50 ማር10፥38፤ ዮሐ19፥30
12፥53 ሚክ7፥6፤

12፥31 *መንግሥት ፈልጉ፤* ቍ32 እንደሚያመለክተው፣ ኢየሱስ ይናገር የነበረው ወደ መንግሥቱ ለገቡ አማኞች ስለሆነ፣ ይህ ትእዛዝ ክርስቲያኖች በዚህ ዓለም ካለው ሀብት ይልቅ፣ የእግዚአብሔርን መንግሥት መንፈሳዊ በረከት መፈለግ እንዳለባቸው የሚያሳስብ ነው (ከማቴ 6፥33 ጋር ያነጻጽሩ)።

12፥33 *ለድኾች ስጡ፤* የብልጥግና መዘዝንና ለድኾች የመስጠትን አስፈላጊነት ማስተማር፣ በሉቃስ ወንጌል ዐበይት ሐሳቦች ናቸው (3፥11፤ 6፥30፤ 11፥41፤ 14፥13-14፤16፥9፤ 18፥22፤ 19፥8)።

12፥37 *በአጭር ይታጠቃ... ያስተናግዳቸዋል፤* ጌታው ተገልጋይ በመሆን ፈንታ፣ አገልጋዮቹን አገለገለ (ከ22፥27፤ ማር 10፥45፤ ዮሐ 13፥4-5፡12-16 ጋር ያነጻጽሩ)።

12፥38 *በሁለተኛውም ሆነ በሦስተኛው ክፍል፤* ሮማውያን ሌሊቱን ለአራት ሲከፍሉት (ማር 13፥35)፣ አይሁዳውያን ግን ለሦስት ይከፍሉታል (መሳ 7፥19) ፤ የማቴ 14፥25 ማብ ይመ፤ እነዚህ ምናልባት የአይሁድ የመጨረሻዎቹ ሁለት የሌሊት ክፍሎች ሊሆኑ ይችላሉ፤ ግብዣው የጀመረውም ከሌሊቱ በመጀመሪያው ክፍል ሊሆን ይችላል።

*12፥40፤* ክርስቶስ መቼ እንደሚመጣ አይታወቅም እንጂ፣ ተመልሶ እንደሚመጣ ግን እርግጥ ነው (ከማቴ 24፥36 ጋር ያነጻጽሩ)።

*12፥41፤* ኢየሱስ ሕዝቡን በተምሳሌት ያስተምራቸው እንጂ፣ ደቀ መዛሙርቱን የሚያስተምራቸው ግን በግልጽ ነው፣ ሆኖም እዚህ ላይ ነቅተው መጠበቅ እንዳለባቸው በማስጠንቀቅ የተናገረው ለደቀ መዛሙርቱ ብቻ አልነበረም (ማር 13፥37 ይመ)። በሚቀጥሉት ቍጥሮችም፣ ኀላፊነትን መወጣት ምን ያህል አስፈላጊ እንደ ሆነ በአጽንዖት ገልጸአል።

12፥42 *ብልህ መጋቢ፤* ትጉሕ የሆነ አገልጋይ (ቍ43)፣ የንብረት ሁሉ ኀላፊ እንዲሆን ይሾም ነበር (16፥1 ይመ)።

12፥46-48 *ይቈራርጠዋል... ክፉኛ ይገረፋል...በጥቂቱ ይገረፋል፤* እያንዳንዱ ሰው በተሰጠው መብት መጠንና መብቱንም በተጠቀመበት ልክ፣ ዳኛው የሚፈርድበት ሦስት የቅጣት ደረጃዎች ናቸው (ሮሜ 2፥12-16 ይመ)።

12፥49 *እሳት፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ በተለያየ ዐይነት ተለዋጭ ዘይቤ ተጠቅሶ ይገኛል (የ3፥16 ማብ ይመ)። እዚህ ላይ ፍርድንና (ቍ 49) መለያየትን (ቍ 51)የሚያመለክት ነው። ከጽድቅ በተለዩ ክፉዎች ላይ ፍርድ ተበይኖባቸዋል።

12፥50 *ጥምቀት፤* ኢየሱስ በመስቀል ላይ የተቀበለውን መከራ ያመለክታል (የማር 10፥38 ማብ ይመ)። *እስኪፈጸምም ድረስ፤* ኢየሱስ፣ በመስቀል ላይ መከራ መቀበሉ ቢቀር ይወድ ነበር፤ ሆኖም ግን በመስቀል ላይ ሆኖ መከራውን በመቀበል፣ "ተፈጸመ አለ" (ዮሐ19፥28-30)

12፥51 *ለመለያየት፤* የማቴ 10፥34 ማብ ይመ።

አማት በምራቷ ላይ፣ ምራትም በአማቷ ላይ ተነሥተው ይለያያሉ።”

## ዘመናትን መመርመር

[54]ደግሞም ለሕዝቡ እንዲህ አለ፤ “ደመና በምዕራብ በኩል ሲወጣ ስታዩ ወዲያው፣ ዝናብ ሊመጣ ነው ትላላችሁ፤ እንደዚያም ይሆናል፤ [55]የደቡብ ነፋስም ከደቡብ በኩል ሲነፍስ፣ ቀኑ ሞቃት ይሆናል ትላላችሁ፤ እንደዚያም ይሆናል። [56]እናንት ግብዞች፤ የምድሩንና የሰማዩን መልክ መመርመር ታውቁበታላችሁ፤ ታዲያ ይህን የአሁኑን ዘመን መመርመር እንዴት ተሳናችሁ?

[57]“ታዲያ ራሳችሁ ትክክለኛ የሆነውን ነገር ለምን አትፈርዱም? [58]ከባላጋራህ ጋር ወደ ዳኛ ፊት ለመቅረብ ስትሄድ፣ ገና በመንገድ ላይ ሳለህ ለመታረቅ ጥረት አድርግ፤ አለበለዚያ ጐትቶ ወደ ዳኛው ይወስድሃል፤ ዳኛውም ለመኰንኑ አሳልፎ ይሰጥሃል፤ መኰንኑም ወደ ወህኒ ይጥልሃል፤ [59]እልሃለሁ፤ የመጨረሻዋን ሳንቲም[a] እስክትከፍል ድረስ ከዚያ አትወጣም።

## የንስሓ ጥሪ

**13** በዚህ ጊዜ መጥተው፣ ጲላጦስ ደማቸውን ከመሥዋዕታቸው ጋር ስለ ደባለቀው ስለ ገሊላ ሰዎች ያወሩለት ሰዎች በዚያ ነበሩ። [2]እርሱም እንዲህ መለሰላቸው፤ “ታዲያ እነዚህ የገሊላ ሰዎች ይህ ሥቃይ የደረሰባቸው ከሌሎቹ የገሊላ ሰዎች ሁሉ ይልቅ ኀጢአተኞች ስለ ነበሩ ይመስላችኋል? [3]አይደለም እላችኋለሁ፤ ንስሓ ካልገባችሁ ሁላችሁ እንደዚሁ ትጠፋላችሁ። [4]ወይም ደግሞ በሰሊሆም ግንብ ተንደባቸው የሞቱት ዐሥራ ስምንት ሰዎች በኢየሩሳሌም ከሚኖሩት ሰዎች ሁሉ ይልቅ በደለኞች ስለ ነበሩ ይመስላችኋል? [5]አይደለም፤ እላችኋለሁ፤ ንስሓ ካልገባችሁ ሁላችሁ እንደዚሁ ትጠፋላችሁ።”

[6]ደግሞም እንዲህ ሲል ይህን ምሳሌ ተናገረ፤ “አንድ ሰው በወይኑ ዕርሻ ቦታ የተተከለች አንዲት የበለስ ተክል ነበረችው፤ እርሱም ፍሬ ሊፈልግባት መጥቶ ምንም አላገኘም። [7]የወይን አትክልት ሠራተኛውንም፣ ‘እነሆ፤ ፍሬ ለማግኘት ልፈልግባት ሦስት ዓመት ወደዚህች በለስ መጥቼ ምንም አላገኘሁም፤ ስለዚህ ቍረጣት፤ ለምን ዐፈሩን በከንቱ ታሟጥጣለች?’ አለው።

[8]“እርሱ ግን እንዲህ ሲል መለሰለት፤ ‘ጌታ ሆይ፤ ዙሪያዋን እስክኰተኵትላትና ፍግ እስከማደርግላት ድረስ ለዘንድሮ ብቻ ተዋት፤ [9]ለከርሞ ካፈራች መልካም ነው፤ አለበለዚያ ትቈርጣታለህ።’ ”

## አንዲት ጐባጣ ሴት በሰንበት ቀን ተፈወሰች

[10]ኢየሱስ በሰንበት ቀን በአንድ ምኵራብ ያስተምር ነበር። [11]በዚያም የድካም መንፈስ ዐሥራ ስምንት ዓመት ሙሉ አካለ ስንኩል ያደረጋት አንዲት ሴት ነበረች፤ እርሷም ከመጕበጧ የተነሣ ፈጽሞ ቀና ማለት አትችልም ነበር። [12]ኢየሱስም ባያት ጊዜ ጠራትና፣ “አንቺ ሴት፤ ከሕመምሽ ነጻ ወጥተሻል” አላት፤ [13]እጁንም በላይዋ ጫነ፤ እርሷም ወዲያው ቀጥ ብላ ቆመች፤ እግዚአብሔርንም አመሰገነች።

[14]የምኵራቡ አለቃ ግን፣ ኢየሱስ በሰንበት ቀን ስለ ፈወሰ ተቈጥቶ ሕዝቡን፣ “ሥራ ሊሠራባቸው የሚገባ ስድስት ቀኖች አሉ፤ ስለዚህ በእነዚያ ቀኖች እየመጣችሁ ተፈወሱ እንጂ፣ በሰንበት ቀን አይደለም” አላቸው።

[15]ጌታም መልሶ እንዲህ አለው፤ “እናንተ ግብዞች፤ ከእናንተ መካከል አንድ ሰው በሬውን ወይም አህያውን በሰንበት ቀን ከማደሪያው ፈትቶ ውሃ ሊያጠጣ ይወስደው የለምን?

[a]59 ግሪኩ ሌፕቶን ይላል

ማቴ10፥21
12፥54 ማቴ16፥3
12፥58 ማቴ5፥25
12፥59 ማቴ5፥26፤ ማር12፥42
13፥1 ማቴ27፥2
13፥2 ዮሐ9፥2፡3
13፥4 ዮሐ9፥7፡11
13፥5 ማቴ3፥2፤ ሐሥ 2፥38
13፥6 ኢሳ5፥2፤ ኤር8፥13፤ ማቴ21፥19
13፥7 ማቴ3፥10
13፥10 ማቴ4፥23
13፥11 ቍ16
13፥13 ማር5፥23
13፥14 ዘፀ20፥9፤ ማቴ12፥2፤ማር5፥22
13፥15 ሉቃ14፥5

*12፥54-56፤* በምዕራብ በኩል የሚመጣው ነፋስ ከሜድትራኒያን ባሕር የሚነሣ ሲሆን፣ በደቡብ በኩል የሚመጣው ደግሞ ከምድረ በዳ ነው። ሰዎች የአየሩን ሁኔታ ለመናገር እንዲህ ያሉትን ምልክቶችን መጠቀም ቢችሉም፣ የመንፈሳዊ ሕይወት ድቀትን፣ የመሲሑ መምጣትና ተሠቃይቶ መሞቱን፣ ከሮማውያን ጋር የሚደረገውን ፍጥጫና እነዚህ ሁኔታዎች በእነርሱ ሕይወት ላይ የሚያስከትሉትን ዘላለማዊ ዕጣ ፈንታ ማስተዋል አልቻሉም።

12፥57 *ራሳችሁ... አትፈርዱም?* ፈሪሳውያን ባየቀበሉትም፣ የሮም አስተዳደር ባይደግፈውም፣ ቤተ ሰብም ጫና ቢያደርግ እያንዳንዱ ሰው በእግዚአብሔር አምኖ ለመኖር መወሰን አለበት። በእስራኤል ሕዝብ ላይ ፍርድ ከመድረሱ በፊት፣ እያንዳንዱ ሰው በአፋጣኝ ውሳኔ ሊያደርግ እንደሚገባው የወቅቱ ሁኔታ ያሳስብ ነበር።

12፥58 *ለመታረቅ... አለበለዚያ፤* ጊዜ ከማለፉ በፊት፣ ዕዳን መክፈል ያስፈልጋል።

13፥1 *ገሊላ ሰዎች፤* እዚህ ላይ የተጠቀሰው ሁኔታ በዝርዝር አይታወቅ እንጂ፣ በቤተ መቅደስ መሥዋዕት በማቅረብ ላይ እንዳሉ የተገደሉት ሰዎች ሁኔታ ከጲላጦስ ድርጊት ጋር የተያያዘ ነው። እነዚህ የገሊላ ሰዎች፣ ለዚህ አሠቃቂ ሞት የተዳረጉት ምናልባት የሮምን ሕግ ጥሰው በመገኘታቸው ሊሆን ይችላል።

13፥2፡4 *ከሌሎቹ... ይልቅ ኀጢአተኞች... በደለኞች፤* በዚያን ዘመን፣ መቅሠፍት የሚደርሰው፣ እጅግ ኀጢአተኛ በሆኑ ሰዎች ላይ ብቻ ነው ተብሎ ይታመን ነበር (ዮሐ 9፥1-2፤ ይመ፤ እንዲሁም ኤልፋዝ አላግባብ ኢዮብን የከሰሰበትን ኢዮ 4፥7፤ 22፥5 ይመ)። ኢየሱስ ግን ሰዎች ሁሉ ኀጢአተኞች በመሆናቸው ንስሓ ሊገቡ እንደሚገባቸውና አለበለዚያ ግን የማያመልጡት ፍርድ እንደ ሚጠብቃቸው ተናገረ።

13፥4 *ዐሥራ ስምንት ሰዎች፤* ታሪኩ በዝርዝር የማይታወቅ ነው። *በሰሊሆም ግንብ፤* በኢየሩሳሌም ቅጥር ውስጥ በደቡብ ምሥራቅ በኩል የተገነባ ነው።

13፥6 *የበለስ ተክል፤* የእስራኤልን ሕዝብ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (የማር 11፥14 ማብ ይመ)፤ በሌላ በኩልም እያንዳንዱን ሰው ሊያመለክት ይችላል።

13፥7 *ሦስት ዓመት፤* ተክሎች ፍሬ ለማፍራት የሚያስችላቸው በቂ ጊዜ ነበር።

13፥11 *መንፈስ... አካለ ስንኩል ያደረጋት፤* ክፉ መናፍስት በሰዎች ላይ ልዩ ልዩ ሕመም ያደርሳሉ (የ4፥33 ማብ ይመ)፤ ስለ ሴትየዋ በሽታ የተሰጠው ገለጻ የሚያመለክተው ሕመም ያለባት በወገቧ ላይ መሆኑን ነው።

13፥12 *ከሕመምሽ ነጻ ወጥተሻል፤* ክፉውን መንፈስ አስወጥቶ፣ ሴትየዋንም ከሰይጣን እስራትና ከጕባጣነቷ ነጻ አወጣት።

13፥14 *በሰንበት ቀን ስለ ፈወሰ፤* በኢየሱስ ላይ ተቃውሞ የቀረበው፣በሰንበት ዕለት ስለ አከናወነው ድርጊት ነበር (16፥6-11፤ 14፥1-6፤ ማቴ 12፥1-8፡11-12፤ ዮሐ 5፥1-8፤ በተጨማሪም ዘፀ 20፥9-10 ይመ)። *የምኵራቡ አለቃ፤* የ8፥41 ማብ ይመ።

13፥15 *በሬውን... ፈትቶ፤* ለሰው ከማሰብ ይልቅ፣ ለእንስሳ ይበልጥ ይጨነቁ ነበር። ኢየሱስ ከሳሾቹን “ግብዞች” አላቸው፤ ምክንያቱም ለሕግ ከፍተኛ ቦታ የሚሰጡ ቢመስሉም፣ ዐላማቸው

[16]ታዲያ፣ ይህች ሴት የአብርሃም ልጅ ሆና ሳለች ዐሥራ ስምንት ዓመት ሙሉ በሰይጣን ታስራ ስትኖር፣ ከዚህ እስራት በሰንበት ቀን መፈታት አይገባትምን?”

[17]ይህን በተናገረ ጊዜ ተቃዋሚዎቹ ሁሉ ዐፈሩ፤ ሕዝቡ ሁሉ ግን እርሱ ባደረገው ድንቅ ሥራ ሁሉ ደስ አላቸው።

## የሰናፍጭ ቅንጣትና የእርሾ ምሳሌ

13፥18፡19 ተጓ ምብ - ማር 4፥30-32
13፥18-21 ተጓ ምብ - ማቴ13፥31-33

[18]ከዚያም ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ “የእግዚአብሔር *መንግሥት* ምን ትመስላለች? ከምንስ ጋር ላመሳስላት? [19]አንድ ሰው ወስዶ በአርሻው ውስጥ የዘራትን የሰናፍጭ ቅንጣት ትመስላለች፤ አድጋ ዛፍ ሆነች፤ የሰማይ ወፎችም በቅርንጫፎቿ ላይ ሰፈሩ።”

[20]ደግሞም እንዲህ አለ፤ “የእግዚአብሔርን *መንግሥት* ከምን ጋር ላመሳስላት? [21]አንዲት ሴት ወስዳ በሙሉ እስኪቦካ ድረስ በዛ ካለ[ሀ] ዱቄት ጋር የደባለቀችውን እርሾ ትመስላለች።”

## ጠባቧ በር

[22]ከዚያ በኋላ ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም እያመራ ሳለ፣ በሚያልፍባቸው ከተሞችና መንደሮች እያስተማረ ያልፍ ነበር። [23]አንድ ሰውም ቀርቦ፣ “ጌታ ሆይ፤ የሚድኑት ጥቂት ሰዎች ብቻ ናቸውን?” አለው።

እርሱም እንዲህ አላቸው፤ [24]“በጠባቧ በር ለመግባት ተጋደሉ፤ እላችኋለሁ፤ ብዙዎች ለመግባት ይፈልጋሉ ነገር ግን አይሆንላቸውም፤ [25]የቤቱ ባለቤት ተነሥቶ በሩን ከቈለፈ በኋላ በውጭ ቆማችሁ፣ ‘ጌታ ሆይ፤ ክፈትልን’ እያላችሁ በሩን ማንኳኳት ትጀምራላችሁ።

“እርሱ ግን፣ ‘ማን እንደ ሆናችሁና ከየት እንደ መጣችሁ አላውቅም’ ብሎ ይመልስላችኋል።

[26]“እናንተም፣ ‘ከአንተ ጋር አብረን በልተናል፣ ጠጥተናል፤ በአደባባያችንም አስተምረሃል’ ትላላችሁ።

[27]“እርሱም፣‘እላችኋለሁ፤ ማን እንደሆናችሁና ከየት እንደመጣችሁ አላውቅም፤ እናንት ዐመፀኞች ሁሉ ከእኔ ራቁ’ ይላል።

[28]“አብርሃምን፣ ይስሐቅንና ያዕቆብን፣ ነቢያትንም ሁሉ በእግዚአብሔር *መንግሥት* ውስጥ ስታዩ፣ እናንተ ግን ወደ ውጭ ተጥላችሁ ስትቀሩ በዚያን ጊዜ ልቅሶና ጥርስ ማፋጨት ይሆናል። [29]ሰዎች ከምሥራቅ፣ ከምዕራብ፣ ከሰሜንና ከደቡብ መጥተው በእግዚአብሔር *መንግሥት* በማእድ ይቀመጣሉ። [30]እነሆ፤ ከኋለኞች መካከል ፊተኞች የሚሆኑ፣ ከፊተኞች መካከልም ኋለኞች የሚሆኑ አሉ።”

## ኢየሱስ ስለ ኢየሩሳሌም ዐዘነ

13፥34፡35 ተጓ ምብ – ማቴ 23፥37-39
13፥34፡35 ማመ – ሉቃ 19፥41

[31]በዚያን ጊዜ ከፈሪሳውያን አንዳንዶች መጥተው፣ “ሄሮድስ ሊገድልህ ስለሚፈልግ ተነሥተህ ከዚህ ሂድ” አሉት።

[32]እርሱም እንዲህ አላቸው፤ “ሄዳችሁ ለዚያ ቀበሮ፣ ‘እነሆ፤ ዛሬና ነገ አጋንንትን አወጣለሁ፤ ሕመምተኞችን እፈውሳለሁ፤ በሦስተኛውም ቀን ከግቤ እደርሳለሁ’ ብላችሁ ንገሩት፤ [33]ይሁን እንጂ ነቢይ ከኢየሩሳሌም ውጭ ይሞት ዘንድ አይገባምና ዛሬና ነገ፣ ከነገ ወዲያም ወደዚያው ጕዞዬን እቀጥላለሁ።

13፥16 ማቴ4፥10፤ ሉቃ3፥8
13፥17 ኢሳ66፥5
13፥18 ማቴ3፥2፤ 13፥24
13፥19 ማቴ13፥32፤ ሉቃ17፥6
13፥21 1ቆሮ5፥6
13፥22 ሉቃ9፥51
13፥24 ማቴ7፥13
13፥25 ማቴ7፥23፤ 25፥10–12
13፥27 ማቴ 7፥23
13፥28 ማቴ8፥12
13፥29 ማቴ8፥11
13፥30 ማቴ19፥30
13፥31 ማቴ14፥1
13፥32 ዕብ2፥10
13፥33 ማቴ21፥11

[ሀ]21 ግሪኩ *ሦስት መስፈሪያ* (22 ሊትር የሚያህል) ይላል

እርሱንና የሚያደረገውን ፈውስ መቃወም ነበር።

13፥19 *የሰናፍጭ ቅንጣት፤* የማቴ 13፥31-32፤ ማር 4፥31 ማብ ይመ። ቅዱሳት መጻሕፍት፣ ዛፎች አንዳንድ ጊዜ የሕዝብ ትእምርት ናቸው (ሕዝ 17፥23፤ 31፥6፤ ዳን 4፥12፡21 ይመ)።

13፥21 *እርሾ፤* የማቴ 13፥33 ማብ ይመ፤ ትንሹ እርሾ፣ ሊጡን በሙሉ ሊያቦካ እንደሚችል በአጽንዖት ተገልጸአል፤ የእግዚአብሔር መንግሥት ምን ያህል የመለወጥ ኀይል እንዳለው ከዚህም ተምሳሌት መገንዘብ ይቻላል። *ብዛት ባለው፤* (አማራጭ ትርጕሙን ይመ) በዘፍ 18፥6 ላይ እንደ ተገለጸው ሣራ የወሰደችውን ያህል ማለት ነው (ያንኑ አማራጭ ትርጕም ይመ)።

13፥22 *በሚያልፍባቸው ከተሞችና መንደሮች፤* የኢየሱስን ሕይወት የሚያመለክተውን 1475 ይመ፤ በ11፥1 እና በ13፥21 ላይ በሚገኘው ታሪክ መካከል፣ ኢየሱስ ይሁዳን ለቆ በፔሪያና አካባቢዋ አገልግሎቱን ጀመረ፤ ይህም በ13፥22-19፥27፤ በማቴ 19፥1-20፡28፤ በማር 10ና በዮሐ 10፥40-42 ላይ ተጽፎ ይገኛል። በፔሪያ በነበረው የመጨረሻ አገልግሎቱ፣ በሰሜን በኩል ወደ ገሊላ ሄዶ፣ ከዚያም እንደ ገና ወደ ደቡብ በመጓዝ በፔሪያ አድርጎ ወደ ኢያሪኮና ወደ ኢየሩሳሌም የሄደ ይመስላል። ኢየስስ በፔሪያ አገልግሎቱ ያስተማረው ትምህርት ነው በማለት ሉቃስ የጻፈውን፣ ማቴዎስ ከፔሪያ ውጪ ኢየሱስ ባስተማረው ምንባብ ውስጥ ጽፎታል (7፥13-14፡22-23)፤ ምናልባት ኢየሱስ በተለያዩ አጋጣሚዎች የተናገራቸውን ልዩ ልዩ አባባሎች ከሉቃስ በተለየ ሁኔታ ደጋግሞ ያቀረበ ይመስላል። *ወደ ኢየሩሳሌም እያመራ፤* የመስቀልን ሞት ወደሚቀበልበት ከተማ ማለት ነው። ኢየሱስ በፔሪያ አገር ቢያስተ ምርም፣ ትኵረት ያደረገው ግን ቅድስቲቱ ከተማ ላይና ሊቀበለው ባለው መከራ ላይ ነበር።

13፥23 *የሚድኑት ጥቂት ... ናቸውን?* የኢየሱስን ትምህርት ለመስማትና ለመፈወስ የመጡት ሰዎች አያሌ ቢሆኑም፣ በታማኝነት ኢየሱስን ይከተሉ የነበሩት ሰዎች ጥቂቶች ብቻ መሆናቸውን፣ ጠያቂው ያስተዋለው ይመስላል፤ ኢየሱስም ጥያቄውን በቀጥታ አልመለሰም፤ ነገር ግን ጊዜው ካለፈ በኋላ ብዙ ሰዎች ወደእርሱ መንግሥት ለመግባት እንደሚሞክሩ ተናገረ።

13፥27 *ማንም እንደሆናችሁ ... አላውቅም፤* ማቴ 7፥23፤ 25፥12 ይመ።

13፥29 *ሰዎች ከምሥራቅ፣ ከምዕራብ፣ ከሰሜንና ከደቡብ፤* ከአራቱ ማእዘናት (መዝ 103፥3) አሕዛብንም ጨምሮ ከሁሉም ሕዝቦች ማለት ነው።

13፥31 *ሄሮድስ ሊገድልህ ስለሚፈልግ፤* የማቴ 14፥1 ማብ ይመ። በዚህ ጊዜ ኢየሱስ የሄሮድስ ግዛት በሆነው በፔሪያ አገር ነበር (የ3፥1 ማብ ይመ)። ኢየሱስ ይህን አገር ለቆ ወደ ይሁዳ እንዲሄድ፣ ፈሪሳውያን ሊያስፈራሩት ሞከሩ።

13፥32 *ቀበሮ፤* ተንኰለኛ አውሬ ነው። *ዛሬና ነገ፤* ይህ ሐረግ፣ በሴም ቋንቋ መቼ እንደሆነ ያልታወቀን፣ ነገር ግን ውሱን ወቅ ትን ያመለክታል። *ከግቤ እደርሳለሁ፤* ኢየሱስ እንዲያከናውነው፣ አስቀድሞ የተወሰነ ዕቅድ ስላለው፣ ዐላማው እስኪፈጸም ድረስ ምንም ዐይነት ጕዳት ሊደርስበት አይችልም (ከ4፥43፤ 9፥22 ጋር ያነጻጽሩ)።

13፥33 *ከኢየሩሳሌም ውጭ፤* ኢየሱስ መከራ የሚቀበልበት ጊዜ ገና አልደረሰም ነበር (2፥38፤ ዮሐ 7፥30፤ 8፥20 ይመ፤ ከዮሐ 8፥59፤ 10፥39፤ 11፥54 ጋር ያነጻጽሩ)። ብዙ ነቢያት በኢየሩሳሌም እንደ ሞቱ ሁሉ፣ እርሱም በኢየሩሳሌም ውስጥ ይገደላል።

[34]"ኢየሩሳሌም፣ ኢየሩሳሌም ሆይ፤ ነቢያትን የምትገድዪ፣ ወደ አንቺ የተላኩትንም በድንጋይ የምትወግሪ! ዶሮ ጫጩቶቿን በክንፎቿ ሥር እንደምትሰበስብ፣ ልጆችሽን ለመሰብሰብ ስንት ጊዜ ፈለግሁ፤ እናንተ ግን እምቢ አላችሁ፤ [35]እነሆ፤ ቤታችሁ ወና ሆኖ ቀርቶአል:: እላችኋለሁ፤ በጌታ ስም የሚመጣ የተባረከ ነው እስክትሉ ድረስ ከእንግዲህ አታዩኝም::"

## ኢየሱስ በአንድ ፈሪሳዊ ቤት

14፥8-10 ማመ – ምሳ 25፥6:7

**14** አንድ ሰንበት ቀን፣ ኢየሱስ ምግብ ሊበላ ከፈሪሳውያን አለቆች አንዱ ወደ ነበረ ሰው ቤት በገባ ጊዜ፣ ሰዎች በዐይን ይከታተሉት ነበር:: [2]በዚያም በአካል እብጠት የሚሠቃይ አንድ ሰው ከፊት ለፊቱ ነበር:: [3]ኢየሱስም ሕግ ዐዋቂዎችንና ፈሪሳውያንን፣ "በሰንበት ቀን ሕመምተኞችን መፈወስ ተገቢ ነው ወይስ አይደለም?" ሲል ጠየቃቸው:: [4]እነርሱ ግን ዝም አሉ:: እርሱም ሰውየውን ይዞ ፈወሰውና አሰናበተው::

[5]ደግሞም፣ "ከእናንተ አንዱ፣ ልጁ[ m] ወይም በሬው በሰንበት ቀን ጕድጓድ ቢገባበት ፈጥኖ የማያወጣው ማን ነው?" አላቸው:: [6]እነርሱም ለዚህ አንዳች መልስ ሊያገኙ አልቻሉም::

[7]ኢየሱስ ተጋባዦቹ የክብር ስፍራ ሲመርጡ ተመልክቶ፣ እንዲህ ሲል ይህን ምሳሌ ለእነርሱ ነገራቸው፤ [8]"አንድ ሰው ሰርግ ቢጠራህ፣ በክብር ስፍራ አትቀመጥ፤ በክብር ከአንተ የሚበልጥ ሰው ተጠርቶ ከሆነ፣ [9]ሁለታችሁንም የጋበዘው መጥቶ፣ ስፍራውን 'ለዚህ ሰው ልቀቅለት' ይልሃል፤ አንተም እያፈርህ ወደ ዝቅተኛው ስፍራ ትሄዳለህ:: [10]ነገር ግን በተጠራህ ጊዜ ዝቅተኛውን ስፍራ አይተህ ተቀመጥ፤ ጋባዥህም ሲመጣ፣ ወዳጄ ሆይ፤ ወደ ላይ ከፍ በል ይልሃል፤ አንተም በዚያን ጊዜ አብረውህ በማእድ በተቀመጡ ሰዎች ሁሉ ፊት ትከበራለህ:: [11]ምክንያቱም ራሱን ከፍ ከፍ የሚያደርግ ሁሉ ዝቅ ይላል፤ ራሱንም ዝቅ ዝቅ የሚያደርግ ሁሉ ከፍ ይላል::"

[12]ኢየሱስም የጋበዘውን ሰው ደግሞ እንዲህ አለው፤ "የምሳ ወይም የእራት ግብዣ በምታደርግበት ጊዜ፣ በአጸፋው እንዳይጋብዙህና ብድራትን እንዳይመልሱልህ፣ ወዳጆችህን ወይም ወንድሞችህን ወይም ዘመዶችህን ወይም ከበርቴ ጎረቤቶችህን አትጋብዝ። [13]ነገር ግን ግብዣ ባዘጋጀህ ጊዜ ድኾችን፣ አካለ ስንኩሎችን፣ ሽባዎችንና ዐይነ ስወሮችን ጥራ፤ [14]ትባረካለህም:: እነዚህ ብድር ሊመልሱልህ ስለማይችሉ፣ በጻድቃንም ትንሣኤ ብድራትህ ይመለስልሃል::"

## የትልቅ ግብዣ ምሳሌነት

14፥16-24 ማመ - ማቴ 22፥2-14

[15]ከኢየሱስ ጋር በማእድ ከተቀመጡት መካከል አንዱ ይህን ሰምቶ "በእግዚአብሔር መንግሥት ቀርቦ ከማእድ የሚበላ ብፁዕ ነው" አለው::

[16]ኢየሱስም እንዲህ አለው፤ "አንድ ሰው ትልቅ ግብዣ አዘጋጅቶ ብዙ ሰው ጠራ፤ [17]የግብዣውም ሰዓት በደረሰ ጊዜ የተጋበዙትን እንግዶች፣ እነሆ፤ ሁሉም ነገር ተዘጋጅቶአልና ኑ ብሎ እንዲጠራ አገልጋዩን ላከባቸው::

13፥34 ማቴ23፥27
13፥35 መዝ118፥26 ኤር12፥17፤22፥5፤ ሉቃ19፥38
14፥1 ማቴ12፥10፤ ሉቃ7፥36፤11፥37
14፥3 ማቴ12፥2፤ 22፥35
14፥5 ሉቃ13፥15
14፥7 ሉቃ11፥43
14፥11 ማቴ23፥12
14፥13 ቍ21
14፥14 ሐሥ24፥15
14፥15 ኢሳ25፥6፤ ማቴ3፥2፤26፥29፤ ሉቃ13፥29፤ራእ19፥9

[m]5 አንዳንድ ቅጆች *አህያው* ይላሉ

13፥34 *ስንት ጊዜ፤* በተመሳሳይ ወንጌላት ከተገለጸው በላይ፣ ኢየሱስ በኢየሩሳሌም ብዙ ጊዜ እንደ ነበር ይህ ሰቈቃ ያመለክታል (ከዮሐ 2፥13፤4፥45፤ 5፥1፤7፥10፤ 10፥22 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ሆኖም በቍ 34-35 ያለው ሐሳብ የተነገረው ከኢየሩሳሌም ራቅ ብሎ በሚገኘው ፔሪያ በሚባል አገር ነው፤ በማቴ 23፥37-38 ላይ በተጻፈው መሠረት፣ ይህ የሆነው በሕማማቱ ሳምንት ማክሰኞ ዕለት ነው:: ኢየሱስ አብዛኛውን ትምህርቱንና ቃሉን ደጋግሞ አስተምሯል::

13፥35 *ቤታችሁ ወና ሆኖ፤* እግዚአብሔር፣ ቤተ መቅደሱንና የእርሱ የሆነችውን ከተማ ይተዋታል (21፥20:24፤ ኤር 12፥7፤ 22፥5 ይመ):: *እስክትሉ ድረስ ከእንግዲህ አታዩኝም፤* ዘካ 12፥10፤ ራእ 1፥7 ይመ፤ ከኢሳ 45፥23፤ ሮም 14፥11፤ ፊል 2፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ::

14፥1 *አንድ ሰንበት ቀን፤* በሰንበት ቀን ከተደረጉት ሰባት ታምራት መካከል፣ ሉቃስ የጻፈው አምስቱን ብቻ ነው (4፥31:38፤ 6፥6፤ 13፥14፤ 14፥1)፤ የተቀሩት ሁለቱ በዮሐ 5፥10፤ 9፥14 ላይ ይገኛሉ:: ፈሪሳውያን በሰንበት ዋዜማ ስለሚያደርጉት ዝግጅት የ13፥14 ማብ ይመ:: ለሰንበት ቀን የሚያስፈልገው ምግብ የሚዘጋጀው በዋዜማው ነበር::

14፥2 *በአካል እብጠት፤* የሰውነት ክፍልን የጎዳ ሕመም መኖሩን የሚያመለክት፣ ፈሳሽ የቋጠረ በሽታ ነው::

14፥3 *ሕግ ዐዋቂዎችንና* የ5፥17፤ 7፥30 ማብ ይመ:: ኢየሱስ ታምር ከማድረጉ በፊት ይህን ጥያቄ በመጠየቅ፣ በኋላ ተቃውሞ ሊያቀርቡ የሚችሉበትን መንገድ ዘጋባቸው::

14፥5 *ልጁ፤* (አማራጭ ትርጕሙን ይመ)፤ በዘዳ 5፥14 ላይ ለሰውና ለእንስሳ በተናጠል ሕግ ተቀምጧል፤ ይኸውም፣ "ልጅህ" በማለትና "በሬህ" በማለት ይጀምራል:: አንዳንድ ጥንታዊ ቅጆች ልጅህ በማለት ፈንታ "አህያው" ይላሉ፤ "አህያው" የሚለው "በሬው ጕድጓድ ውስጥ ቢገባበት" ከሚለው ጋር የሚጣጣም ነው:: ኢየሱስ ያደረገው ታምር፣ በመምህራኑ አተረጓጐም ሕግን መተላለፍ ይመስላል፣ ይሁን እንጂ፣ የሙሴ ሕግ፣ ኢየሱስ ያደረገውን መልካም ሥራ አይከለክልም::

14፥7 *የክብር ስፍራ፤* ሰው የክብርን ስፍራ ለማግኘት ያለው ፍላጎት ምን ያህል አስቸጋሪ እንደሆነ፣ ኢየሱስ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ባደረገው የመጨረሻ እራት ላይ ታይቷል (22፥24)::

14፥11 *ራሱንም ዝቅ ዝቅ የሚያደርግ ሁሉ ከፍ ይላል፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በተደጋጋሚ የተነገረ መሠረታዊ ሐሳብ ነው (11፥43፤ 18፥14፤ 20፥46፤ 2ዜና 7፥14-15፤ ምሳ 3፥34፤ 25፥6-7፤ ማቴ 18፥4፤ 23፥12፤ ያዕ4፥10፤ 1ጴጥ 5፥6 ይመ)::

14፥14 *በጻድቃንም ትንሣኤ፤* ሰዎች ሁሉ ከሙታን ይነሣሉ (ዳን 12፥2፤ ዮሐ 5፥28-29፤ ሐሥ 24፥15)፤ አንዳንዶች የጻድ ቃንን ትንሣኤ (1ቆሮ 15፥23፤ 1ተሰ 4፥16፤ ራእ 20፥4-6)፣ ከአጠቃላይ ትንሣኤ የተለየ ነው ይላሉ (1ቆሮ 15፥12:21፤ ዕብ 6፥2፤ ራእ 20፥11-15):: *በጻድቃንም፤* በክርስቶስ ቤዛዊ ሞት፣ እግዚአብሔር ጻድቃን ያላቸውና፣ እምነታቸው በሥራቸው የተመሰከረላቸው ናቸው (ከማቴ 25፥34-40 ጋር ያነጻጽሩ)::

14፥15 *በእግዚአብሔር መንግሥት... ከማእድ የሚበላ፤* ወደ ፊት የሚመጣው የመሲሑ ታላቅ ግብዣ ነው፤ የሚመጣውን መንግሥት ከግብዣ ጋር አዛምዶ ማመልከት የተለመደ ነው (13፥29፤ ኢሳ 25፥6፤ ማቴ 8፥11፤ 25፥1-10፤ 26፥29፤ ራእ 19፥9)::

14፥16 *ኢየሱስም እንዲህ አለው፤* ሰውየው የሰጠውን አስተያየት እንደ ጥሩ አጋጣሚ በመጠቀም፣ ሁሉ ሰው ወደ መንግሥተ ሰማያት እንደማይገባ የሚያስጠነቅቅ ተምሳሌት ተናገረ::

18“ነገር ግን ሁሉም የየራሳቸውን ምክንያት ይፈጥሩ ጀመር፤ አንደኛው፣ ገና አሁን መሬት ስለ ገዛሁ ሄጄ ማየት አለብኝ፤ እባክህ፣ ይቅርታ አድርግልኝ አለው::

19“ሌላኛውም፣ ‘አምስት ጥማድ በሬዎች ገዝቻለሁ፤ እነርሱን ልፈትናቸው ስለ ሆነ እባክህ ይቅርታ አድርግልኝ’ አለ::

20“ሌላው ደግሞ፣ ‘ገና ሙሽራ ስለሆንሁ ልመጣ አልችልም’ አለ::

21“አገልጋዩም ተመልሶ መጥቶ ይህንኑ ለጌታው ነገረው:: በዚህን ጊዜ የቤቱ ጌታ ተቈጥቶ አገልጋዩን፣ ‘ቶሎ ብለህ ወደ ከተማው አውራ ጐዳናዎችና መተላለፊያ መንገዶች ውጣ፤ ድኾችንና አካለ ስንኩሎችን፣ ዐይነ ስውሮችንና ዐንካሶችን ወደዚህ አስገባቸው’ አለው::

22“አገልጋዩም፣ ‘ጌታዬ፤ ያዘዝኸው ሁሉ ተፈጽሟል፤ ገና አሁንም ቦታ አለ’ አለው::

23“ጌታውም አገልጋዩን፣ ‘ወደ ጐዳናዎችና ወደ ገጠር መንገዶች ውጣ፤ ቤቴም እንዲሞላ ያገኘኸውን ሁሉ በግድ አምጥተህ አስገባ፤ 24እላችኋለሁና ከተጋበዙት ከእነዚያ ሰዎች መካከል አንድ ሰው እንኳ ግብዣዬን አይቀምስም አለው::”

## ደቀ መዝሙር መሆን የሚያስከፍለው ዋጋ

25ብዙ ሕዝብ አብሮት እየተጓዙ ሳለ፣ ኢየሱስ ዘወር ብሎ እንዲህ አላቸው፤ 26“ወደ እኔ የሚመጣ ሁሉ አባቱንና እናቱን ሚስቱንና ልጆቹን፣ ወንድሞቹንና እኅቶቹን፣ የራሱንም ሕይወት እንኳ ሳይቀር ባይጠላ፣ ደቀ መዝሙሬ ሊሆን አይችልም፤ 27የራሱንም መስቀል ተሸክሞ የማይከተለኝ ደቀ መዝሙሬ ሊሆን አይችልም::

28“ከእናንተ አንድ ሰው ሕንጻ ለመሥራት ቢፈልግ፣ መደምደም መቻል አለመቻሉን በመጀመሪያ ተቀምጦ ዋጋውን የማይተምን ማን ነው? 29መሠረቱን ጥሎ መደምደም ቢያቅተው፣ ያዩት ሁሉ ይዘባበቱበታል፤ 30እንዲህም ይላሉ፤ ‘ይህ ሰው ማነጽ ጀምሮ ነበር፤ መደምደም ግን አቃተው::’

31“ወይም አንድ ንጉሥ ከሌላው ንጉሥ ጋር ጦርነት ሊገጥም በሚነሣበት ጊዜ፣ ሃያ ሺህ ሰራዊት አስከትቶ የሚመጣበትን ንጉሥ፣ በዐሥር ሺህ ሰራዊት መመከት እንደሚችል ተቀምጦ የማይመክር ማን ነው? 32መቋቋም የማይችል ከሆነ፣ ሌላው ንጉሥ ገና ሩቅ ሳለ፣ መልእክተኞች ልኮ ዕርቅ ይጠይቃል:: 33እንደዚሁም፣ ከእናንተ ማንም ያለውን ሁሉ የማይተው፣ ደቀ መዝሙሬ ሊሆን አይችልም::

34“ጨው መልካም ነው፤ ጨው ጣዕሙን ካጣ ግን እንዴት ተመልሶ የጨውነት ጣዕም ሊኖረው ይችላል?

35ለመሬትም ሆነ ለማዳበሪያነት የማይጠቅም በመሆኑ ወደ ውጭ ይጣላል::

“ሰሚ ጆሮ ያለው ይስማ::”

## የጠፋው በግ ምሳሌ

15፥4-7 ተጓ ምብ – ማቴ 18፥12-14

**15** አንድ ቀን፣ ቀረጥ ሰብሳቢዎችና “ኃጢአተኞች” ሁሉ ሊሰሙት በዙሪያው ተሰበሰቡ:: 2ፈሪሳውያንና ጸሐፍትም፣ “ይህ ሰው ኀጢአተኞችን ይቀበላል፤ ከእነርሱም ጋር ይበላል” እያሉ አጕረመረሙ::

3ኢየሱስም እንዲህ ሲል ይህን ምሳሌ ነገራቸው፤ 4“ከእናንተ መካከል አንዱ መቶ በጎች ቢኖሩትና ከእነርሱ አንዱ ቢጠፋበት፣ ዘጠና ዘጠኙን በሜዳ ላይ ጥሎ የጠፋውን እስኪያገኝ ድረስ ሊፈልገው የማይሄድ ማን ነው? 5ባገኘውም ጊዜ ደስ ብሎት በጫንቃው ተሸክሞ፣ 6ወደ ቤቱ ይመለሳል፤ ወዳጆቹንና ጎረቤቶቹንም በአንድነት ጠርቶ፣ ‘የጠፋውን በጌን አግኝቻለሁና ከእኔ ጋር ደስ ይበላችሁ’ ይላቸዋል:: 7እላችኋለሁ፤ እንደዚሁም ንስሓ ከማያስፈልጋቸው ከዘጠና ዘጠኝ ጻድቃን ይልቅ፣ ንስሓ በሚገባ በአንድ ኀጢአተኛ በሰማይ ደስታ ይሆናል::

14፥21 ቍ13
14፥24 ማቴ21፥43፤ሐሥ 13፥46
14፥26 ማቴ10፥37፤ዮሐ12፥25
14፥27 ማቴ10፥38፤ሉቃ9፥23
14፥33 ፊል3፥7፡8
14፥34 ማር9፥50
14፥35 ማቴ5፥13፤ማቴ11፥15
15፥1 ሉቃ5፥29
15፥2 ማቴ9፥11
15፥3 ማቴ13፥3
15፥4 መዝ23፤119፥176፤ኤር31፥10፤ሕዝ34፥11-16፤ሉቃ5፥32፤19፥10
15፥6 ቍ9
15፥7 ቍ10
15፥9 ቍ6
15፥10 ቍ7
15፥11 ማቴ21፥28

14፥18 *መሬት ስለ ገዛሁ፤* ሰውየው የመጀመሪያውን ጥሪ ተቀብሎ ይሆናል (ቍ 16)፤ የመጨረሻው ጥሪ ሲቀር ብለት ግን (እንደ አይሁድ ልማድ የግብዣው ዝግጅት ሲጠናቀቅ ማለት ነው)፣ ለሌሎች ፍላጎቶቹ ቅድሚያን ሰጠ፤ ከቀረቡት ምክንያቶች ውስጥ፣ አንዳቸውም እንኳ እውነተኛ አልነበሩም፤ ለምሳሌ፣ ማንም ሰው ቢሆን የዕርሻውን ቦታ ሳያይ ወይም በሬ ዎችን አስቀድሞ ሳይሞክር አይገዛም (ቍ 19)::

14፥24 *ከተጋበዙት... ሰዎች፤* አይሁዳውያን የእግዚአብሔርን ጥሪ ችላ ቢሉ፣ ከእግዚአብሔር መንግሥት እንደሚወገዱና በምትካቸውም አሕዛብ ወደ መንግሥቱ እንደሚገቡ ኢየሱስ አስጠነቀቀ (20፥9-19 ይመ)::

14፥26 *አባቱንና... ባይጠላ፤* ማንም ሰው ከቅርብ ቤተ ሰቡ አብልጦ ኢየሱስን መውደድ እንዳለበት የሚያመለክት አባባል ነው (ይህን ዘይቤ በተመለከተ ሚል 1፥2-3 ይመ)፤ በተጨማሪም ማቴ 10-37 ይመ::

14፥27 *መስቀል ተሸክሞ፤* 9፥23፤ ማቴ 10፥38 እና ማብ ይመ::

14፥28 *ዋጋውን የማይተምን፤* ማንኛውም ሰው በረከትን ብቻ በመናፈቅ፣ ሳያስተውል እንዲከተለው ኢየሱስ አይፈልግም:: አንድ ቤተ ሠሪ ወጪውን እንደሚተምን ወይም አንድ ንጉሥ የጦር ኀይሉን ጥንካሬ እንደሚመዝን ሁሉ (ቍ 31)፣ አንድ ክርስቲያንም ኢየሱስ ከተከታዮቹ ምን እንደሚፈልግ ሊያስተውል ይገባዋል::

14፥33 *ያለውን ሁሉ የማይተው፤* ኢየሱስ ከአንድ አማኝ የሚጠይቀው ዋጋ፣ ራስን ሙሉ በሙሉ መስጠትን ነው::

14፥34 *ጨው መልካም ነው፤* የማር 9፥50 ማብ ይመ::

15፥1 *ቀረጥ ሰብሳቢዎችና “ኀጢአተኞች”፤* የ3፥12፤ ማር 2፥15 ማብ ይመ::

15፥2 *አጕረመረሙ፤* ድምፃቸውን አሰምተው ሳይሆን፣ እርስ በርሳቸው ነው:: *ከእነርሱም ጋር ይበላል፤* ከአንድ ሰው ጋር አብሮ መብላት፣ ከተራ ግንኙነት የሚበልጥና ሰውዬውን ማክበር ያመለክታል (ከሐሥ 11፥3፤ 1ቆሮ 5፥11፤ ገላ 2፥12 ጋር ያነጻጽሩ)::

15፥3 *ይህን ምሳሌ፤* ኢየሱስ ለፈሪሳውያን ጕርምርምታ መልስ የሰጠው፣ የእግዚአብሔርን ፍቅር ከእነርሱ ግንኙነት ጋር በማነጻጸር ነው::

15፥4 *የጠፋውን፤* ስለ በጎች እረኛ የተነገረው ይህ ዐቢይ ሐሳብ፣ በመዝ 23፤ ኢሳ 40፥11፤ ሕዝ 34፥11-16 ላይም ይገኛል::

15፥7 *ንስሓ ከማያስፈልጋቸው ...ጻድቃን፤* ንስሓ መግባት አያስፈልግም ለሚሉ፣ ለፈሪሳውያንና ለሕግ መምህራን፣ በምፀት የተነገረ ቃል ሳይሆን አይቀርም:: *በሰማይ ደስታ፤* አንድ ኀጢአተኛ ንስሓ ሲገባ፣ እግዚአብሔር በርኅራኄና በደስታ ሲቀበለው፣ ፈሪሳውያንና የሕግ መምህራን ግን እንዴት እንደሚመለከቱት የሚያነጻጽር ነው (ቍ 2)::

## የጠፋው ሳንቲም ምሳሌ

8“ወይም ዐሥር የብር ሳንቲሞች ያላት ሴት ከዐሥሩ አንዱ ቢጠፋባት፣ እስክታገኘው ድረስ መብራት አብርታ፣ ቤቷን ጠርጋ፣ አጥብቃ የማትፈልግ ሴት ማን ናት? 9ባገኘችውም ጊዜ ወዳጆቿንና ጐረቤቶቿን፣ በአንድነት ጠርታ፣ ‘የጠፋብኝን የብር ሳንቲም አግኝቻለሁና ከእኔ ጋር ደስ ይበላችሁ’ ትላቸዋለች:: 10እላችኋለሁ፤ እንደዚሁም ንስሓ በሚገባ በአንድ ኀጢአተኛ በእግዚአብሔር መላእክት ፊት ደስታ ይሆናል::

## ጠፍቶ የተገኘው ልጅ ምሳሌነት

11ደግሞም ኢየሱስ እንዲህ አላቸው፤ “አንድ ሰው ሁለት ልጆች ነበሩት:: 12ከእነርሱም ታናሹ ልጅ አባቱን፣ ‘አባቴ ሆይ፤ ከሀብትህ ድርሻዬን ስጠኝ’ አለው፤ አባትየውም ሀብቱን ለልጆቹ አካፈላቸው::

13“ብዙም ቀን ሳይቈይ፣ ታናሹ ልጅ ድርሻውን ሁሉ ጠቅልሎ ወደ ሩቅ አገር ሄደ፤ በዚያም በማጋጣነት ንብረቱን አባከነ:: 14እርሱም ያለውን ሁሉ ከጨረሰ በኋላ፣ በዚያ አገር ሁሉ ጽኑ ራብ ሆነ፤ ይቸገርም ጀመር:: 15ስለዚህ ከዚያ አገር ነዋሪዎች አንዱን ተጠጋ፤ ሰውየውም ዐሣማ እንዲቀልብለት ወደ ዕርሻው ላከው:: 16ዐሣማዎቹ የሚመገቡትን ዐሠር እንኳ ለመብላት ይመኝ ነበር፤ ነገር ግን ይህን እንኳ የሚሰጠው ሰው አልነበረም::

17“ልብ በገዛ ጊዜ ግን እንዲህ አለ፤ ‘ስንቱ የአባቴ ሠራተኛ ምግብ ተርፎታል፤ እኔ ግን እዚህ በራብ ልሞት ተቃርቤአለሁ! 18ተነሥቼ ወደ አባቴ ልሂድና፣ እንዲህ ልበለው፤ “አባቴ ሆይ፤ በሰማይና በአንተ ፊት በድያለሁ፤ 19ከእንግዲህ ልጅህ ተብዬ ልጠራ አይገባኝም፤ ከተቀጠሩት አገልጋዮችህ እንደ አንዱ ቍጠረኝ::’ 20ስለዚህም ተነሥቶ ወደ አባቱ ሄደ::

“ነገር ግን፣ እርሱ ገና ሩቅ ሳለ፣ አባቱ አይቶት ራራለት፤ ወደ እርሱም እየሮጠ ሄዶ ዐቅፎ ሳመው::

21“ልጁም፣ ‘አባቴ ሆይ፤ በሰማይና በአንተ ፊት በድያለሁ፤ ከእንግዲህ ልጅህ ተብዬ ልጠራ አይገባኝም’ አለው::+

22“አባቱ ግን አገልጋዮቹን እንዲህ አላቸው፤ ‘ፈጥናችሁ ከሁሉ ምርጥ የሆነውን ልብስ አምጡና አልብሱት፤ ለጣቱ ቀለበት፣ ለእግሩም ጫማ አድርጉለት፤ 23የሰባውንም ፍሪዳ አምጡና ዕረዱ፤ እንብላ፤ እንደሰት፤ 24ይህ ልጄ ሞቶ ነበር፤ አሁን ግን ሕያው ሆኖ አለ፤ ጠፍቶም ነበር፤ ተገኝቶአል::” ከዚያም ይደሰቱ ጀመር::

25“በዚህ ጊዜ ታላቁ ልጅ በዕርሻ ቦታ ነበረ፤ ከዚያም ተመልሶ ወደ ቤት በተቃረበ ጊዜ፣ የሙዚቃና የጭፈራ ድምፅ ሰማ፤ 26እርሱም ከአገልጋዮቹ አንዱን ጠርቶ ነገሩ ምን እንደ ሆነ ጠየቀው:: 27አገልጋዩም፣ ‘ወንድምህ መጥቶአል፤ በሰላም በጤና ስለ መጣም አባትህ የሰባውን ፍሪዳ ዐርዶለታል’ አለው::

28“ታላቅ ወንድሙም ተቈጣ፤ ወደ ቤትም መግባት አልፈለገም፤ አባቱም ወደ ውጭ ወጥቶ እንዲገባ ለመነው:: 29እርሱ ግን መልሶ አባቱን እንዲህ አለው፤ ‘እነሆ፤ ይህን ያህል ዘመን እንደ ባሪያ አገለግዬሃለሁ፤ ከትእዛዝህም አንዱን እንኳ አላጓደልሁም፤ አንተ ግን ከባልንጀሮቼ ጋር እንድደሰት አንዲት የፍየል ግልገል እንኳ አልሰጠኸኝም፤ 30ነገር ግን ይህ ልጅህ ንብረትህን ከጋለሞቶች ጋር አውድሞ ሲመጣ፣ የሰባውን ፍሪዳ አረድህለት::’

31“አባቱም እንዲህ አለው፤ ‘ልጄ ሆይ፤ አንተ ሁልጊዜ ከእኔ ጋር ነህ፤ የእኔ የሆነው ሁሉ የአንተ ነው፤ 32ይህ ወንድምህ ግን ሞቶ ነበር፤ ሕያው ሆነ፤ ጠፍቶ ነበር ተገኘ፤

15፥12 ቍ30፤ ዘዳ21፥17
15፥13 ቍ30፤ ሉቃ16፥1
15፥15 ዘሌ11፥7
15፥18 ዘሌ26፥40፤ ማቴ3፥2
15፥20 ዘፍ45፥14፡ 15፥46፥29፤ሐሥ 20፥37
15፥21 መዝ51፥4
15፥22 ዘፍ41፥42፤ ዘካ3፥4፤ራእ6፥11
15፥24 ቍ32፤ኤፌ 2፥1፡5፤5፥14፤ 1ጢ5፥6
15፥28 ዮና4፥1
15፥30 ቍ12፡13፤ ምሳ29፥3
15፥32 ቍ24፤ ሚል3፥17

+21 አንዳንድ የጥንት ቅጆች *ከተቀጠሩት አገልጋዮችህ እንኳ እንደ አንዱ ቍጠረህ ተቀበለኝ* የሚል አላቸው

15፥8 *ዐሥር የብር ሳንቲሞች፤* በግሪካውያን ዘንድ ዳርካማ በመባል የሚታወቀው ሳንቲም ከሮማውያን ዲናር ጋር የተቀራረበ ዋጋ ያለው ሲሆን፣ የአንድ ቀን የሥራ ክፍያ ዋጋ ነበር (ማቴ 20፥2):: *አጥብቃ የማትፈልግ ...?* በቅርብ ምሥራቅ ያሉ ቤቶች መስኮት የሌላቸውና ወለላቸውም ዐፈር በመሆኑ፣ የጠፋን ዕቃ ፈልጎ ማግኘት ቀላል አይደለም::

15፥12 *ከሀብትህ ድርሻዬን፤* አባትየው የሚያወርሳቸውን ሀብት አከፋፍሉ (ለታላቅ ልጅ ዕጥፍ፤ ዘዳ 21፥17 ይመ፤ የሉቃ 12፥13 ማብ ይመ) ነገር ግን ለራሱ እስከ ሕይወቱ ፍጻሜ ድረስ የሚያስፈልገውን ያስቀረ ይመስላል፤ ይሁን እንጂ ታናሹ ልጅ በጠየቀው መሠረት፣ በውርስ የሚያገኘውን ድርሻ አስቀድሞ መስጠት የተለመደ አይደለም::

15፥13 *ድርሻውን ሁሉ ጠቅልሎ፤* ከአባቱ በውርስ ያገኘውን፣ ልጁ ጠቅልሎ የሄደበት ዐላማ ግልጽ ነው፤ ይህም ዐላማ ወደቤቱ እንደገና ላለመመለስና ከወላጆቹ ቍጥጥር ነጻ በመሆን ያገኘውን ሀብት እንደፈለገ ሊጠቀምበት አስቦ ነው:: *በማጋጣነት፤* ታላቅ ወንድሙ በመናደዱ ምክንያት አጋኖ ቢናገርም በቍ 30 ላይ በግልጽ ተብራርቷል::

15፥15 *ዐሣማ እንዲቀልብለት፤* ለአንድ አይሁዳዊ፣ ይህ የመጨረሻው የተዋረደ ሥራ ከመሆኑም በላይ፣ ዐሣማ እንደ ርኩስ እንስሳ ይቈጠር ነበር (ዘሌ 11፥7)::

15፥16 *ዐሠር፤* ለእንስሳት የሚሰጥ የእህል ገለባ ነው::

15፥22-23፤ *ምርጥ የሆነውን ልብስ...ቀለበት ...ጫማ... እንብላ፤* እያንዳንዱ ስጦታ፣ ማዕረግንና ተቀባይነት ማግኘትን ያመለክታል (ከዘፍ 41፥42፤ ዘካ 3፥4 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይኸውም፣ ረጅሙ ልብስ ከፍተኛ ማዕረግን፣ ማኅተም ያለበት ቀለበት ሥልጣንን፣ ጫማው ደግሞ ልጅነትን (ባሪያዎች ያለ ጫማ ይሄዱ ነበር)፣ የሰባውም ፍሪዳ ልዩ በዓልን ያመለክታል::

15፥28 *ታላቅ ወንድሙም፤* የአባትየው ይቅር ባይ ፍቅር፣ የእግዚአብሔርን መለኮታዊ ምሕረት ሲያሳይ፣ ጥላቻ የተሞላው የወንድምየው ሁኔታ ደግሞ፣ ኢየሱስን የሚቃወሙትን የፈሪሳውያንና የሕግ መምህራንን ሁኔታ ያመለክታል::

15፥29 *አንዲት የፍየል ግልገል እንኳ፤* ከሰባ ፍሪዳ ጋር ሲነጻጸር፣ በዝቅተኛ ደረጃ የሚታይ ምግብ ነው::

15፥30 *ይህ ልጅህ፤* ጥላቻው ከፍተኛ በመሆኑ፣ እንደ ወንድሙ እንኳ አልቈጠረውም::

15፥31 *የእኔ የሆነው ሁሉ የአንተ ነው፤* አባትየው ለሁለቱም ወንድማማቾች እኩል ፍቅር አለው፤ ስለዚህ ይህ ምሳሌ፣ ‘የጠፋው ልጅ” ከሚባል “የአባት ፍቅር” ቢባል ይሻላል፤ ይህ ምሳሌ፣ የእግዚአብሔርን ፍቅር ከራስ ወዳድነታቸው የተነሳ ለመረዳት ያልቻሉትን ፈሪሳውያንን፣ አንድ ኀጢአተኛ ንስሓ ሲገባ በእግዚአብሔር ዘንድ ከሚኖረው ደስታ ጋር በማነጻጸር ያሳያል::

15፥32 *ሞቶ ነበር ሕያው ሆነ፤* የታናሹ ልጅ ወደ አባቱ መመለስ፣ ሥዕላዊ በሆነ አገላለጽ ክርስቲያናዊ መለወጥን ያመ

| የኢየሱስ ተምሳሌቶች | | | |
|---|---|---|---|
| ተምሳሌት | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ |
| ከዕንቅብ በታች ያከለ መብራት | 5÷14-15 | 4÷21-22 | 8÷16፤ 11÷33 |
| ብልሁና ሰነፉ ቤት ሠሪዎች | 7÷24-27 | | 6÷47-49 |
| አዲስ ልብስ በአሮጌ ዕራፊ ላይ | 9÷16 | 2÷21 | 5÷36 |
| አዲስ የወይን ጠጅ በአሮጌ አቍማዳ | 9÷17 | 2÷22 | 5÷37-38 |
| ዘሪውና ዘር የወደቀባቸው መሬቶች | 13÷3-8፡ 18-23 | 4÷3-8፡ 14-20 | 8÷5-8፡ 11-15 |
| ዐረሞች | 13÷24-3፡ 36-43 | | |
| የሰናፍጭ ቅንጣት | 13÷31-32 | 4÷30-32 | 13÷18-19 |
| እርሾ | 13÷33 | | 13÷20-21 |
| የተደበቀ ሀብት | 13÷44 | | |
| ውድ የሆነ ዕንቍ | 13÷45-46 | | |
| መረብ | 13÷47-50 | | |
| ባለ ንብረት | 13÷52 | | |
| የጠፋው በግ | 18÷12-14 | | 15÷4-7 |
| ዐመፀኛው አገልጋይ | 18÷23-34 | | |
| ሁለት ወንዶች ልጆች | 20÷1-16 | | |
| የወይን ቦታው ሠራተኞች | 21÷28-32 | | |
| የወይን ዕርሻ ገበሬዎች | 21÷33-44 | 12÷1-11 | 20÷9-18 |
| የሰርግ ግብዣ | 22÷2-14 | | |
| የበለስ ዛፍ | 24÷32-35 | 13÷28-29 | 21÷29-31 |
| ታማኝና ልባም አገልጋይ | 24÷45-51 | | 12÷42-48 |
| ዐሥሩ ቈነጃጅት | 25÷1-13 | | |
| ታላንት | 25÷14-30 | | 19÷12-27 |
| በጎችና ፍየሎች | 25÷31-46 | | |
| የሚበቅለው ዘር | | 4÷26-29 | |
| ትጕሑ አገልጋይ | | 13÷35-37 | 12÷35-40 |
| ገንዘብ አበዳሪ | | | 7÷41-43 |
| ደጉ ሳምራዊ | | | 10÷30-37 |
| እወነተኛ ባልንጀራ/ወዳጅ | | | 11÷5-8 |
| ሰነፉ ባለ ጠጋ/ሀብታም | | | 12÷16-21 |
| የማታፈራዋ በለስ (ፍሬ አልባዋ) | | | 13÷6-9 |
| በግብዣ ዝቅተኛ ስፍራ | | | 14÷7-14 |
| ታላቅ እራት | | | 14÷16-27 |
| የደቀ መዝሙርነት ዋጋ | | | 14÷28-33 |
| የጠፋው ድሪም | | | 15÷8-10 |
| የጠፋው ልጅ | | | 15÷11-32 |
| ዐመፀኛው መጋቢ | | | 16÷1-8 |
| ባለ ጋው ሰውና አልዓዛር | | | 16÷19-31 |
| ...ያው | | | 17÷7-10 |
| ...መበለት | | | 18÷2-8 |
| ...ፕ ሰብሳቢው | | | 18÷10-14 |

ስለዚህ ደስ ሊለንና ፍሥሐ ልናደርግ ይገባናል::" '

## የብልጉ መጋቢ ምሳሌነት

**16** ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አለ፤ "አንድ ሀብታም ሰው አንድ መጋቢ ነበረው፤ ይኸው መጋቢ የሀብታሙን ሰው ንብረት እንደሚያባክን ለዚሁ ሀብታም ሰው ወሬ ደረሰው:: [2]ስለዚህ አስጠራውና፣ 'ይህ የምሰማብህ ምንድን ነው? ከእንግዲህ አንተ መጋቢ ልትሆነኝ ስለማትችል፣ የምታስተዳድረውን ንብረት መቈጣጠሪያ ሒሳብ አስረክበኝ' አለው::

[3]"መጋቢውም በልቡ እንዲህ አለ፤ 'ጌታዬ ከመጋቢነት ሊሽረኝ ነው፤ ለማረስ ጕልበት የለኝም፤ መለመን ደግሞ ዐፍራለሁ፤ ስለዚህ ምን ላድርግ? [4]ከመጋቢነት የተሻርሁ እንደ ሆነ ሰዎች በቤታቸው እንዲቀበሉኝ የማደርገውን ዐውቃለሁ::'

[5]"ስለዚህ የጌታው ዕዳ ያለባቸውን ሰዎች እያንዳንዳቸውን ጠራ፤ የመጀመሪያውንም ሰው 'የጌታዬ ዕዳ ምን ያህል አለብህ?' አለው::

[6]"እርሱም፣ 'አንድ መቶ ማድጋ* ዘይት አለብኝ' አለ::

"መጋቢውም፣ 'የውል ወረቀትህን እንካ፤ ቶሎ ተቀምጠህ "አምሳ ማድጋ" ብለህ ጻፍ' አለው::

[7]"ከዚያም ሌላውን፣ 'አንተስ ስንት አለብህ?' አለው::

"እርሱም፣ 'አምሳ ዳውላ† ስንዴ' አለው::

"መጋቢውም፣ 'የብድር ደብዳቤህን እንካ፤ "አርባ ዳውላ" ብለህ ጻፍ' አለው::

[8]ጌታውም አጭበርባሪውን መጋቢ በብልኀነቱ አደነቀው፤ የዚህ ዓለም ልጆች ከመሰሎቻቸው ጋር በሚኖራቸው ግንኙነት ከብርሃን ልጆች ይልቅ ብልኆች ናቸውና:: [9]ስለዚህ እላችኋለሁ፤ 'የዚህ ዓለም ገንዘብ ባለቀ ጊዜ በዘላለም ቤት ተቀባይነት እንዲኖራችሁ፣ በዚሁ ገንዘብ ወዳጆችን ለራሳችሁ አፍሩበት::

[10]"በትንሽ ነገር ታማኝ የሆነ በትልቁም ይታመናል፤ በትንሽ ነገር ያልታመነ በትልቁም አይታመንም:: [11]እንግዲህ፣ በዚህ ዓለም ሀብት ካልታመናችሁ፣ እውነተኛውንማ ሀብት ማን ዐደራ ብሎ ይሰጣችኋል? [12]በሌላው ሰው ሀብት ካልታመናችሁ፣ የራሳችሁ የሆነውን ሀብት ማን ይሰጣችኋል?

[13]"በአንድ ጊዜ ሁለት ጌቶችን ማገልገል የሚችል ማንም ባሪያ የለም፤ አንዱን ጠልቶ ሌላውን ይወዳል፤ ወይም አንዱን ይጠጋል፤ ሌላውን ይንቃል:: የእግዚአብሔርም የገንዘብም ባሪያ መሆን አትችሉም::"

[14]ገንዘብ የሚወዱ ፈሪሳውያን ይህን ሁሉ ሰምተው በኢየሱስ አፌዙበት:: [15]እርሱም እንዲህ አላቸው፤ "እናንተ በሰዎች ፊት ራሳችሁን የምታጸድቁ ናችሁ፤ እግዚአብሔር ግን ልባችሁን ያውቃል፤ በሰዎች ዘንድ የከበረ፣ በእግዚአብሔር ፊት የረከሰ ነውና::

[16]"ሕግና ነቢያት እስከ ዮሐንስ ድረስ ሲነገሩ ኖረዋል፤ ከዚያ በኋላ ግን የእግዚአብሔር መንግሥት የምሥራች ተሰብኮአል፤ ሰውም ሁሉ ወደዚያ ለመግባት ይሻማል:: [17]ነገር ግን ከሕግ አንዲት ነጥብ ከምትወድቅ ሰማይና ምድር ቢያልፍ ይቀላል::

[18]"ሚስቱን ፈቶ ሌላይቱን የሚያገባ ሁሉ ያመነዝራል፤ ከባሏ የተፋታችውንም ሴት የሚያገባ ያመነዝራል::"

16፥1 ሉቃ15፥30:30
16፥8 መዝ17፥14፤ መዝ18፥26፤ ዮሐ12፥36፤ ኤፌ5፥8፤ 1ተሰ5፥5
16፥9 ቈላ11:13፤ ማቴ19፥21፤ ሉቃ12፥33
16፥10 ማቴ25፥21:23፤ ሉቃ19፥17
16፥11 ቈላ9:13
16፥13 ቈላ9:11 ፤ማቴ6፥24
16፥14 ሉቃ23፥35፤1ጢሞ3፥3
16፥15 ሉቃ10፥29፤ራእ2፥23
16፥16 ማቴ4፥23፤5፥17፡11፥12:13
16፥17 ማቴ5፥18
16፥18 ማቴ5፥31:32፤19፥9፤ማር10፥11 ሮሜ7፥2:3፤ 1ቆሮ 7፥10:11

*6 ምናልባት *3 ሺህ ሊትር ይሆናል*
†7 ምናልባት *35 ሺህ ሊትር ይሆናል*

ለክታል (ሮሜ 6፥13፤ ኤፌ 2፥1:5 ይመ):: "ጠፍቶ ነበር ተገኘ" የሚለው ሐረግ፣ "ሞቶ ነበር ሕያው ሆነ" ማለትም ነው (19፥10፤ ማቴ 10፥6፤ 18፥10-14)::

16፥1 *ለደቀ መዛሙርቱ፤* ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት ብቻ ማለት አይደለም (6፥13፤10፥1 ይመ):: *መጋቢ፤* የአንድ ሀብታም ንብረትና ሥራ፣ የበላይ ሆኖ የሚቈጣጠር፣ የሚመራ ማለት ነው:: *እንደሚያባክን፤* የጠፋው ልጅ 'አባካኙ' እንዳደረገው (15፥13)፣ ይህም ሰው የጌታውን ሀብት አባከነ::

16፥3 *ስለዚህ ምን ላድርግ?* እምነት አጕዳይ መጋቢ (ቍ 8)፣ ጌታውን እስከሚያታልል ድረስ፣ ሥልጣኑን ለራሱ ጥቅም ሲያውል፣ ኀፍረት አልተሰማውም ነበር:: ከሥራው እንደሚባረር ባወቀ ጊዜም፣ ለጌታው ያለባቸውን ብድር በመቀነስ፣ ተበዳሪዎቹን በመልካም ችሮታው የራሱ ባለዕዳ አደረጋቸው:: ተበዳሪዎቹ ያለባቸው ዕዳ መቀነሱ፣ በራሱ ማጭበርበር ነው ወይም አይደለም በሚለው ላይ ተርጓሚዎች የተለያየ ሐሳብ ያቀርባሉ፤ መጋቢው የሰረዘው ዕዳ፣ በትክክል የጌታው የነበረው አንጡራ ሀብት ነው? ወይስ በሙሴ ሕግ መሠረት "ወገንህ ከሆነው አይሁድ ትርፍ አትጠይቅ" (ዘዳ 23፥19) የሚለውን በመተላለፍ፣ የጌታውን ባለዕዳዎች ከመጠን በላይ ወለድ ጠይቆአቸው የነበረውን፣ አሁን ይህን ወለድ በመሰረዝ ጌታውን በማያስቀይም ሁኔታ በተበዳሪዎቹ ላይ የነበረውን ዕዳ ቀንሶ ይሆን? በማለት ይጠይቃሉ:: ያም ሆኖ ይህ፣ ሐሳቡ አንድ ነው፤ መጋቢው ሥልጣኑን ለግሉ ተጠቅሞ፣ ለወደፊት ኑሮው ሁኔታዎች አመቻችቶአል::

16፥6 *አንድ መቶ ማድጋ ዘይት፤* የ450 የወይራ ዛፍ ውጤት ማለት ነው::

16፥7 *አምሳ ዳውላ ስንዴ፤* ከአንድ ጋሻ መሬት የሚገኝ ምርት ሊሆን ይችላል::

16፥8 *ከብርሃን ልጆች፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ ማለት ነው (ዮሐ 12፥36፤ ኤፌ 5፥8፤1ተሰ 5፥5)::

16፥9 *የዚህ ዓለም ገንዘብ፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ፣ እግዚአብሔር የሰጣቸውን ማንኛውንም ነገር በአግባብ ለመጠቀም ንቁ መሆን አለባቸው:: *ወዳጆችን... አፍሩበት፤* ለችግረኞች በምድር በጎ ስናደርግ፣ እነርሱ በመንግሥተ ሰማያት በደስታ ይቀበሉናል፤ በዚህ ዐይነት፣ ምድራዊ ሀብትን ጥቅም ላይ ስናውል፣ ዘላለማዊ ዋጋ እናገኛለን::

16፥10 *በትልቁም ይታመናል፤* ከ19፥17፤ ማቴ 25፥21 ጋር ያነጻጽሩ፤ ታማኝነት የሚለካው በዐደራነት በተሰጠው ገንዘብ መጠን ሳይሆን፣ በሚጠቀምበት ሰው ማንነት ነው::

16፥11 *እውነተኛውንማ ሀብት፤* እጅግ ከፍተኛ ዋጋ ያለው፣ መንፈሳዊና የዘላለም የሆነውን ማለት ነው::

16፥13 *ሁለት ጌቶችን፤* ማቴ 6፥24 ይመ፤ ከያዕ 4፥4 ጋር ያነጻጽሩ::

16፥16 *እስከ ዮሐንስ ድረስ፤* የመሲሑን የኢየሱስን መንገድ ያዘጋጀው የመጥምቁ ዮሐንስ አገልግሎት፣ ከአሮጌው ወደ አዲሱ ኪዳን መሸጋገሪያ ነበር (የኤር 31፥31-34፤ ዕብ 8፥6-12 ማብ ይመ):: *ወደዚያ ለመግባት ይሻማሉ፤* የዚህ ሐሳብ ትርጕም አከራካሪ ነው፤ ምናልባት ሰዎች ለእግዚአብሔር መንግሥት ወንጌል ምላሽ ለመስጠት ያሳዩትን ፍላጎት ያመለክት ይሆናል፤ አያሌ ሰዎችም ኢየሱስ የሚያስተላልፈውን መልእክት ለመስማትና ለመቀበል ወደ እርሱ ይመጡ ነበር::

*16፥17፤* የኢየሱስ የአገልግሎት ዘመን አዲሱን የኪዳን ዘመን ያመጣና የአሮጌውን የኪዳን ዘመን ወደ ፍጻሜ ያደረሰ ነው (ከሉቃ 21፥33 ጋር ያነጻጽሩ):: *አንዲት ነጥብ፤* የማቴ 5፥17-18 ማብ ይመ::

16፥18 *ሚስቱን ፈቶ፤* ማቴ 5፥31-32፤ 19፥9፤ ማር 10፥11-12፤ 1ቆሮ 7፥10-11 ይመ:: ጌታ ኢየሱስ፣ ሕግ መከበር እንዳለበት በድጋሚ አረጋገጠ፤ ስለዚህ፣ ዝሙት ምን ጊዜም

## ሀብታሙ ሰውና አልዓዛር

[19]ደግሞም ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ “ሐምራዊና ቀጭን በፍታ የለበሰ፣ በየቀኑም በተድላ ደስታ የሚኖር አንድ ሀብታም ሰው ነበረ። [20]በአንጻሩም፣ መላ ሰውነቱ በቍስል የተወረረ አንድ አልዓዛር የሚባል ድኻ በዚህ ሀብታም ሰው ደጃፍ ይተኛ ነበር፤ [21]ከሀብታሙ ሰው ማእድ የወደቀውን ፍርፋሪ እንኳ ሊመገብ ይመኝ ነበር፤ ውሾችም ሳይቀሩ መጥተው ቍስሉን ይልሱ ነበር።

[22]“ይህም ድኻ ሞተ፤ መላእክትም ወደ አብርሃም ዕቅፍ ወሰዱት። ሀብታሙም ሰው ደግሞ ሞቶ ተቀበረ። [23]በሲኦልም እየተሠቃየ ሳለ ቀና ብሎ ከሩቅ አብርሃምን አየ፤ አልዓዛርንም በዕቅፉ ይዞት አየ። [24]እርሱም፣ ‘አብርሃም አባት ሆይ፤ ራራልኝ፤ በዚህ ነበልባል እየተሠቃየሁ ስለ ሆነ፣ አልዓዛር የጣቱን ጫፍ ውሃ ነክሮ ምላሴን እንዲያቀዘቅዝልኝ እባክህ ላክልኝ’ እያለ ጮኸ።

[25]“አብርሃም ግን እንዲህ አለው፤ ‘ልጄ ሆይ፤ አንተ በምድራዊ ሕይወትህ ዘመን መልካም ነገሮችን እንደ ተቀበልህ፣ አልዓዛርም ደግሞ ክፉ ነገሮችን እንደ ተቀበለ አስታውስ፤ አሁን ግን እርሱ እዚህ ሲጽናና፣ አንተ በሥቃይ ላይ ትገኛለህ። [26]ከሁሉም በላይ ከዚህ ወደ እናንተ ለማለፍ የሚፈልጉ እንደማይችሉ፣ እዚያ ያሉትም ደግሞ ወደ እኛ እንዳይሻገሩ፣ በእኛና በእናንተ መካከል ትልቅ ገደል ተደርጎአል።”

[27]“እርሱም እንዲህ አለ፤ ‘አባት ሆይ፤ እንግዲያውስ አልዓዛርን ወደ አባቴ ቤት እንድትሰደው እለምንሃለሁ፤ [28]አምስት ወንድሞች ስላሉኝ፣ እነርሱም ወደዚህ የሥቃይ ስፍራ እንዳይመጡ ያስጠንቅቃቸው።’

[29]“አብርሃም ግን፣ ‘ሙሴና ነቢያት አሏቸው፤ እነርሱን ይስሙ’ አለው።

[30]“እርሱም፣ ‘አብርሃም አባት ሆይ፤ እንደዚህ አይደለም፤ አንድ ሰው ከሙታን ተነሥቶ ቢሄድላቸው ንስሓ ይገባሉ’ አለ።

[31]አብርሃምም፣ ‘ሙሴንና ነቢያትን የማይሰሙ ከሆነ፣ አንድ ሰው ከሙታን ቢነሣ እንኳ አያምኑም’ አለው።

## ኀጢአት፣ እምነት፣ ኀላፊነት

**17** ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን እንዲህ አላቸው፤ “ሰዎችን የሚያሰናክል መምጣቱ አይቀርም፤ ነገር ግን ለመሰናክሉ መምጣት ምክንያት ለሚሆን ለዚያ ሰው ወዮለት። [2]ይህ ሰው ከእነዚህ ከታናናሾች አንዱን ከሚያሰናክል፣ የወፍጮ ድንጋይ በዐንገቱ ታስሮ ወደ ባሕር ቢጣል ይሻለው ነበር። [3]ስለዚህ ለራሳችሁ ተጠንቀቁ።

“ወንድምህ ቢበድል ገሥጸው፤ ቢጸጸት ይቅር በለው። [4]በቀን ሰባት ጊዜ ቢበድልህና ሰባት ጊዜ፣ ‘ተጸጽቻለሁ’ እያለ ወደ አንተ ቢመለስ ይቅር በለው።”

[5]ሐዋርያትም ጌታን፣ “እምነታችንን ጨምርልን” አሉት።

[6]ጌታም፣ “የሰናፍጭ ቅንጣት የምታህል እምነት ቢኖራችሁ፣ ይህን ሾላ፣ ‘ተነቅለህ ባሕር ውስጥ ተተከል’ ብትሉት ይታዘዛላችኋል” አላቸው።

[7]ደግሞም ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ “ከእናንተ መካከል አንድ ሰው ዐራሽ ወይም በግ ጠባቂ የሆነ አገልጋይ ቢኖረው፣ ከዕርሻ

16፥19 ሕዝ16፥49
16፥20 ሐሥ3፥2
16፥21 ማቴ15፥27፤ ሉቃ15፥16
16፥24 ቍ30፤ ማቴ 5፥22፤ ሉቃ3፥8
16፥25 መዝ17፥14፤ሉቃ6፥21፡ 24፡25
16፥28 ሐሥ2፥40፤ 20፥23፤1ተሰ4፥6
16፥29 ሉቃ4፥17፤ 24፥27፡44 ዮሐ1፥45፤ 5፥45-47፤ ሐሥ15፥21
16፥30 ቍ24፤ ሉቃ3፥8
17፥1 ማቴ5፥29፤ ማቴ18፥7
17፥2 ማቴ5፥29፤ ማር10፥24፤ ሉቃ10፥21
17፥3 ማቴ18፥15፤ ኤፌ4፥32፤ ቈላ3፥13
17፥4 ማቴ18፥21፡22
17፥5 ማር6፥30፤ ሉቃ7፥13
17፥6 ማቴ13፥31፤ 17፥20፤21፥21፤ ማር9፥23፤ ሉቃ13፥19

ርኩሰት ነው፤ ሕግን መተላለፍና ኀጢአት ነው። ማቴዎስም ይህንኑ ሐሳብ በጉልሕ ጽፎአል፤ ይኸውም (1) ፍቺን በተመለከተ ይህ ሕግ የተሰጠው ከሰው የልብ ድንዳኔ የተነሣ ነው፤ (2) ባልና ሚስት ለገቡት የጋብቻ ቃል ኪዳን ታማኞች ሳይሆኑ ሲቀሩ ብቻ ፍች ይፈቀዳል (ማቴ 19፥9)።

16፥19 *ሐምራዊና ቀጭን በፍታ፤* ከፍተኛ ዋጋ የሚያወጣ የልብስ ዐይነት ነው። *አንድ ሀብታም ሰው፤* ለዚህ ሰው ‘ዴቬስ’ የሚል ስያሜ ተሰጥቶታል፤ ይህ ስም በላቲን፣ ‘ሀብታም ሰው’ ማለት ነው።

16፥20 *አልዓዛር፤* ይኸኛው ኢየሱስ ከሞት ያስነሣው የነ ማርታ ወንድም አይደለም (ዮሐ 11፥43-44)። ይህ ምሳሌ ከሆነ፣ ኢየሱስ የተመለከተውን ስም ጠቅሶ የተናገረው እዚህ ላይ ብቻ ነው፤ ሐሳብን አጉልቶ ለማሳየት የቀረበ ሊሆን ይችላል። *በቍስል የተወረረ፤* ይህ ሐረግ በግሪኩ፣ በሕክምና ሙያ የተለመደ አነጋገር ነው፤ በአዲስ ኪዳን ውስጥ የሚገኘውም በዚህ ቍጥር ላይ ብቻ ነው።

16፥22 *ወደ አብርሃም ዕቅፍ፤* በአይሁድ ታልሙድ መጽሐፍ፣ ገነትና (23፥ 43 ይመ) የአብርሃም ዕቅፍ፣ የጻድቃን መኖሪያ እንደ ሆነ ተገልጾአል፤ “የአብርሃም ዕቅፍ” በሞት የተለዩ ጻድቃን ብፅዕናቸውን በትንሣኤ ጊዜ እስከሚያገኙ ድረስ የሚቆዩበት ስፍራ ነው ይባላል።

16፥23 *በሲኦልም፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ የኀጢአትን ስርየት ያልተቀበሉ ሙታን የመጨረሻ ፍርዳቸውን የሚጠብቁበት ቦታ ነው፣ ሥቃዩ የሚጀምረው በሲኦል እንደሆነ ከሀብታሙ ሁኔታ መረዳት ይቻላል። ‘አብርሃም ያለበት’ የተባለው ቦታ የት እንደሆነ በግልጽ አልተገለጸም፤ ይሁን እንጂ ይህ መልካም ማረፊያ፣ ከሲኦል ወደ እርሱ እንዳይመጡም በታላቅ ገደል የተለየ ነው። በገሃነም ያለው ዐይነት ሥቃይ በሲኦልም አለ (እሳት፤ ራእ 20፥10፤ ሥቃይ፤ ራእ 14፥11፤ እንዲሁም ተለይቶ መኖር፤ ማቴ 8፥12)። አንዳንዶች፣ ኢየሱስ፣ አብርሃም ስላለበት ስፍራና ስለ ሲኦል የተናገረውን ሐሳብ ቃል በቃል አይታይም ይላሉ።

16፥28 *አምስት ወንድሞች ስላሉኝ፤* ለመጀመሪያ ጊዜ ሀብታሙ ሰው ለሌሎች መጨነቅ ጀመረ።

16፥29 *ሙሴና ነቢያት፤* ብሉይ ኪዳን ማለት ነው። ሀብታሙ ሰውዬ በሕይወት ሳለ ለቅዱሳት መጻሕፍትና ለሚሰጡት ትምህርት ደንታ ስላልነበረው፣ ወንድሞቹም እንደ እርሱ የሚያደርጉ መሰለው።

16፥30 *አንድ ሰው ከሙታን ተነሥቶ፤* አንድ ሰው ልቡን በማደንደን ቅዱሳት መጻሕፍት የሚሉትን ባይቀበል፣ ምንም ዐይነት ማስረጃ፣ ትንሣኤም እንኳ ቢሆን ሊለውጠው አይችልም።

17፥2 *የወፍጮ ድንጋይ፤* እህል የሚፈጭበት ትልቅ ድንጋይ ነው። *ከእነዚህ ከታናናሾች አንዱን፤* በእምነት ወይም በዕድሜ ወጣት የሆኑትን ማለት ነው (ከ10፥21፤ ማቴ 18፥6፤ ማር 10፥24 ጋር ያነጻጽሩ)።

17፥3 *ወንድምህ፤* ማቴ 18፥15-17 ይመ፤ ከማቴ 12፥50 ጋር ያነጻጽሩ።

17፥4 *ሰባት ጊዜ፤* ይቅርታ ማድረግ ወሰን የሌለው መሆኑን ያመለክታል (ከመዝ 119፥164፤ ማቴ 18፥21-22 ጋር ያነጻጽሩ)።

17፥5 *እምነታችንን ጨምርልን፤* በቍ 1-4 ላይ በተመለከተው መሠረት ራሳቸውን ሲያዩ፣ እምነታቸው ደካማ ሆኖ አገኙት፤ ጌታ ኢየሱስ እንደሚጠብቅባቸው ለመኖር ይችሉ ዘንድ፣ ትልቅ እምነት እንዲኖራቸው ፈለጉ።

*17፥6፤* ማቴ 17፥20፤ ማር 11፥23 ይመ፤ እንዲሁም የማቴ 13፥31-32፤ ማር 4፥31 ማብ ይመ።

17፥7 *አገልጋይ፤* አንድን ተግባር የሚያከናውን ሰው የሚያመለክት ነው (ከ12፥37 ጋር ያነጻጽሩ)።

የተመለሰውን አገልጋዩን፣ 'ቶሎ ወደ ማእድ ቅረብ' ይለዋልን? [8]ከዚህ ይልቅ፣ 'እራቴን እንድበላ አዘጋጅልኝ፣ እኔ እስክበላና እስክጠጣ ድረስ ታጥቀህ አገልግለኝ፤ ከዚያ በኋላ አንተ ደግሞ ትበላለህ፤ ትጠጣለህ' አይለውምን? [9]እንግዲህ ይህ ሰው፣ አገልጋዩ የታዘዘውን በመፈጸሙ መልሶ ያመሰግነዋልን? [10]ስለዚህ እናንተም የታዘዛችሁትን ሁሉ ባደረጋችሁ ጊዜ፣ 'ከቍጥር የማንገባ አገልጋዮች ነን፤ ልናደርገው የሚገባንን ተግባር ፈጽመናል በሉ።'"

## ከለምጽ የነጹ ዐሥር ሰዎች

[11]ከዚህም በኋላ ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም ሲሄድ፣ በሰማርያና በገሊላ ድንበር በኩል ዐለፈ፤ [12]ወደ አንድ መንደር እንደ ገባም ለምጽ* የያዛቸው ዐሥር ሰዎች አገኙት፤ እነርሱም በርቀት ቆመው፣ [13]በታላቅ ድምፅ፣ "ኢየሱስ፤ ጌታ ሆይ፤ ራራልን!" አሉት።

[14]እርሱም ባያቸው ጊዜ፣ "ሂዱና ራሳችሁን ለካህናት አሳዩ" አላቸው። እነርሱም ወደዚያው በመሄድ ላይ ሳሉ ነጹ።

[15]ከእነርሱም አንዱ መፈወሱን ባየ ጊዜ በታላቅ ድምፅ እግዚአብሔርን እያከበረ ተመለሰ፤ [16]በኢየሱስም እግር ላይ በፊቱ ተደፍቶ አመሰገነው፤ ይህም ሰው ሳምራዊ ነበረ።

[17]ኢየሱስም እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ "የነጹት ዐሥር ሰዎች አልነበሩምን? ታዲያ፣ ዘጠኙ የት ደረሱ? [18]ከዚህ ከባዕድ ሰው በስተቀር ተመልሰው እግዚአብሔርን የሚያመሰግኑ የሉም ማለት ነውን?"። [19]ሰውየውንም፣ "ተነሥተህ ሂድ፤ እምነትህ አድኖሃል" አለው።

## የእግዚአብሔር መንግሥት መምጣት

17፥26፡27 ተጓ ምብ – ማቴ 24፥37-39

[20]ፈሪሳውያን የእግዚአብሔር መንግሥት መቼ እንደምትመጣ ኢየሱስን በጠየቁት ጊዜ እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "የእግዚአብሔር መንግሥት በሚታዩ ምልክቶች አትመጣም፤ [21]ሰዎችም፣ 'እዚህ ነው' ወይም 'እዚያ ነው' ማለት አይችሉም፤ እነሆ፤ የእግዚአብሔር መንግሥት በመካከላችሁ† ናትና።"

[22]ለደቀ መዛሙርቱም እንዲህ አላቸው፤ "ከሰው ልጅ ቀኖች አንዱን ለማየት የምትመኙበት ጊዜ ይመጣል፤ ደግሞም አታዩትም። [23]ሰዎች፣ 'እዚያ ነው' ወይም 'እዚህ ነው' ይሏችኋል፤ ተከትላችኋቸውም አትሂዱ፤ [24]ምክንያቱም መብረቅ በርቆ ሰማዩን ከዳር እስከ ዳር እንደሚያበራ፣ የሰው ልጅም በሚመጣበት ቀን ልክ እንደዚሁ ይሆናል። [25]ነገር ግን ይህ ከመሆኑ በፊት የሰው ልጅ ብዙ መሠቃየትና በዚህም ትውልድ መናቅ ይኖርበታል።

[26]"በኖኅ ዘመን እንደ ሆነው ሁሉ፣ በሰው ልጅ ዘመንም እንደዚሁ ይሆናል። [27]ኖኅ ወደ መርከቡ እስከ ገባበት ቀን ድረስ ሰዎች ይበሉና ይጠጡ፣ ያገቡና ይጋቡ ነበር፤ የጥፋትም ውሃ መጥቶ ሁሉንም አጠፋቸው።

[28]"በሎጥ ዘመንም እንዲሁ ነበር፤ ሰዎች ይበሉና ይጠጡ፣ ይገዙና ይሸጡ፣ ተክል ይተክሉና ቤት ይሠሩ ነበር፤ [29]ሎጥ ከሰዶም በወጣበት ዕለት ግን እሳትና ዲን ከሰማይ ዘንቦ በሙሉ አጠፋቸው።

[30]"የሰው ልጅ በሚገለጥበትም ቀን እንደዚሁ ይሆናል። [31]በዚያን ቀን በቤቱ ጣራ ላይ ያለ ማንም ሰው በቤቱ ውስጥ ያለውን ንብረት ለመውሰድ አይውረድ፤ እንዲሁም በዕርሻ ቦታ ያለ ሰው ወደ ኋላው አይመለስ። [32]የሎጥን ሚስት አስታውሱ። [33]ሕይወቱን ለማሰንበት የሚፈልግ ሁሉ ያጣታል፤

*12 የግሪኩ ቃል ከለምጽ ጋር ብቻ የተያያዘ ሳይሆን የተለያዩ የቈዳ በሽታዎችን ለመግለጽ ጥቅም ላይ ይውላል።
†21 ወይም *በውስጣችሁ*

17፥8 ሉቃ12፥37
17፥10 1ቆሮ9፥16
17፥11 ሉቃ9፥51፡52፤ ዮሐ4፥3፡4
17፥12 ዘሌ13፥45፡46፤ ማቴ8፥2
17፥13 ሉቃ5፥5
17፥14 ዘሌ14፥2፤ ማቴ8፥4
17፥15 ማቴ9፥8
17፥16 ማቴ10፥5
17፥19 ማቴ9፥22
17፥20 ማቴ3፥2
17፥21 ቍ23
17፥22 ማቴ8፥20፤ ሉቃ5፥35
17፥23 ማቴ24፥23፤ ሉቃ21፥8
17፥24 ማቴ24፥27
17፥25 ማቴ16፥21፤ ማር13፥30፤ ሉቃ 9፥22፤ 18፥32፤21፥32
17፥26 ዘፍ6፥5-8፤7፥6-24
17፥28 ዘፍ19፥1-28
17፥30 ማቴ10፥23፤16፥27፤24፥3፡27፡37፡39፤25፥31፤ 1ቆሮ1፥7፤1ተሰ 2፥19፤2ተሰ1፥7፤2፥8፤2ጴጥ3፥4፤ ራእ1፥7
17፥31 ማቴ 24፥ 17፡18
17፥32 ዘፍ19፥26
17፥33 ዮሐ12፥25

17፥11 *በሰማርያና በገሊላ ድንበር በኩል፤* ኢየሱስ፣ በስተደቡብ በኩል ወደምትገኘው ኢየሩሳሌም ሲጓዝ፣ በፔሪያ አካባቢ አስተማረ (የ9፥51፤ 13፥22 ማብ ይመ)።

17፥14 *ራሳችሁን ለካህናት አሳዩ፤* አንድ ሰው ከተፈወሰ በኋላ፣ መፈወሱን ለካህን ማሳየት የተለመደ አሠራር ነበር (ዘሌ 13፥2-3፤ 14፥2-32 ይመ)።

17፥16 *ሳምራዊ፤* የ10፥31-33 ማብ ይመ። በመሠረቱ አይሁዳውያን ከሳምራውያን ጋር ኅብረት አያደርጉም ነበር (ዮሐ 4፥9)፤ ሰውየው ከለምጽ መንጻቱ፣ በመካከል የነበረውን የጥል ግድግዳ ጥሶ እንዲመጣ አደረገው (የዘሌ 13፥2፡45-46 ማብ ይመ)።

17፥19 *እምነትህ አድኖሃል፤* ማቴ 4፥22 ይመ።

17፥21 *የእግዚአብሔር መንግሥት በመካከላችሁ ናትና፤* የእግዚአብሔር መንግሥት በዐይን የምትታይ ሳትሆን (ከዮሐ 18፥36 ጋር ያነጻጽሩ)፣ መንፈሳዊ መሆንዋን የሚያሳይ ነው (ማቴ 23፥26)። ነገር ግን አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ (ከ19፥11፤ 21፥7፤ ሐሥ 1፥6 ጋር ያነጻጸሩ)። መንግሥቱ ንጉሡ ኢየሱስ ክርስቶስ ባለበት ቦታ ሁሉ እውን ነው (የ4፥43 ማብ ይመ)። ይሁን እንጂ ዐውደ ምንባቡ (ቍ 20)፣ የእግዚአብሔር መንግሥት መንፈሳዊ መሆኑን በግልጽ ያመለክታል፤ እንግዲህ ይህ አመለካከት ትክክል ከሆነ "በመካከላችሁ" የሚለው ፈሪሳውያንን ብቻ ሳይሆን፣ በአጠቃላይ ሰዎችን ሁሉ ነው።

17፥22 *ለማየት የምትመኙበት፤* በመከራ ጊዜ ክርስቲያኖች፣ ኢየሱስ በክብሩ ወደ ምድር ዳግም መጥቶ ማየትንና ከጭንቀታቸውም ቶሎ እንዲታደጋቸው ይፈልጋሉ።

17፥23 *ተከትላችኋቸውም አትሂዱ፤* ክርስቶስ ዳግም የሚመጣው በዚህ ጊዜ ነው በሚል ትንቢት ተታልላችሁ፣ ሥራችሁን አትተው ማለት ነው።

17፥24 *መብረቅ በርቆ ... እንደሚያበራ፤* የእርሱ ዳግም ምጽአት፣ ድንገተኛና በይፋ የሚታይ ነው (ከ12፥40 ጋር ያነጻጽሩ)።

17፥25 *መሠቃየትና... ይኖርበታል፤* ኢየሱስ ስለ ሞቱ አስቀድሞ በመደጋገም ተናግሮአል (5፥35፤ 9፥22፡43-45፤ 12፥50፤ 13፥32-33፤ 18፥32፤ 24፥7 እንዲሁም 16፥21 ይመ)፤ ይህ ሁሉ በታላቅ ግርማው ዳግም ከመምጣቱ በፊት መፈጸም ነበረበት።

17፥28 *በሎጥ ዘመንም፤* ዘፍ 18፥16-19፥28 ይመ።

17፥30 *የሰው ልጅ በሚገለጥበትም፤* ጌታ ኢየሱስ ዳግም በሚ መጣበት ጊዜ ለሁሉም በግልጽ ይታያል (1ቆሮ 1፥7፤ 2ተሰ 1፥7፤ 1ጴጥ 1፥7፡13፤4-13)።

17፥31 *በቤቱ ጣሪያ ላይ፤* የፓሌስቲና፣ የሙቀት መጠን ከፍተኛ ከመሆኑ የተነሳ፣ በቤት ጣራ ላይ መዝናናት የተለመደ ነበር። የመጨረሻው ጊዜ ሲመጣ በጣራው ላይ ተቀምጦ የነበረው ሰውዬ፣ ንብረቱን ከጥፋት ለማዳን ወደ ቤቱ ለመመለስ ማሰብ አይኖርበትም። ማቴዎስና ማርቆስ በኢየሩሳሌም ላይ ጥፋት ሲመጣ ሽሽት እንደሚኖር የገለጹ ሲሆን፣ በተዘዋዋሪ መልክም ስለ መጨረሻው ዘመን አመልክተዋል (ማቴ 24፥17-18፤ ማር 13፥15)፤ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ግን የኢየሱስን ዳግም ምጽአት የሚመለከት ነው (ቍ 30 ይመ፤ ከ21፥21 ጋር ያነጻጽሩ)።

ሕይወቱን[¶] አሳልፎ የሚሰጥ ግን ያቈያታል። [34]እላችኋለሁ፤ በዚያች ሌሊት ሁለት ሰዎች በአንድ ዐልጋ ይተኛሉ፤ አንዱ ይወሰዳል፤ ሌላው ይቀራል። [35]ሁለት ሴቶች አብረው ይፈጫሉ፤ አንዷ ትወሰዳለች፤ ሌላዋ ትቀራለች። [36]ሁለት ሰዎች በዕርሻ ቦታ አብረው ይሆናሉ፤ አንዱ ይወሰዳል፤ ሌላው ይቀራል።"[¹]

[37]እነርሱም መልሰው፣ "ጌታ ሆይ፤ የሚወሰዱት ወዴት ነው?" አሉት።

እርሱም፣ "ጥንብ ባለበት አሞሮች ይሰበሰባሉ" አላቸው።

## ተግታ የለመነችው መበለት ምሳሌነት

**18** ደቀ መዛሙርቱ ሳይታክቱ ሁልጊዜ መጸለይ እንደሚገባቸው ለማሳየት ኢየሱስ ይህን ምሳሌ ነገራቸው፤ [2]እንዲህም አላቸው፤ "በአንዲት ከተማ የሚኖር እግዚአብሔርን የማይፈራና ሰውን የማያከብር አንድ ዳኛ ነበረ። [3]በዚያችው ከተማ የምትኖር አንዲት መበለት ነበረች፤ እርሷ፣ 'ከባላጋራዬ ጋር ስላለብኝ ጒዳይ ፍረድልኝ' እያለች ወደ እርሱ ትመላለስ ነበር።

[4]"ዳኛውም ለተወሰነ ጊዜ አልተቀበላትም ነበር፤ በኋላ ግን በልቡ እንዲህ አለ፤ 'ምንም እግዚአብሔርን ባልፈራ፣ ሰውንም ባላከብር፣ [5]ይህች መበለት ስለምትጨቀጭቀኝ እፈርድላታለሁ፤ አለበለዚያ ዘወትር እየተመላለሰች ታሰለቸኛለች።'"

[6]ጌታም እንዲህ አለ፤ "ዐመፀኛው ዳኛ ያለውን ስሙ። እግዚአብሔርስ ቀንና ሌሊት ወደ እርሱ ለሚጮኹ ምርጦቹ አይፈርድላቸውምን? ከመጠን በላይስ ችላ ይላቸዋልን? [8]እላችኋለሁ፤ ፈጥኖ ይፈርድላቸዋል፤ ነገር ግን የሰው ልጅ በሚመጣበት ጊዜ በምድር ላይ እምነትን ያገኝ ይሆንን?"

17፥35 ማቴ24፥41
17፥37 ማቴ24፥28
18፥1 ኢሳ40፥31፤ ሉቃ11፥5-8፤ ሐሥ 1፥14፤ ሮሜ1፥10፤ 12፥12፤ኤፌ6፥18፤ ቆላ4፥2፤1ተሰ5፥17
18፥3 ኢሳ1፥17
18፥5 ሉቃ11፥8
18፥6 ሉቃ7፥13
18፥7 ዘዐ22፥23፤ መዝ88፥1፤ ራእ6፥10
18፥8 ማቴ8፥20፤ 16፥27
18፥9 ኢሳ65፥5፤ ሉቃ16፥15
18፥10 ሐሥ3፥1
18፥11 ማቴ6፥5፤ ማር11፥25
18፥12 ኢሳ58፥3፤ ሚል3፥8፤ ማቴ9፥14፤ ሉቃ11፥42
18፥13 ኢሳ66፥2፤ ኤር31፥19፤ ሉቃ 5፥32፤23፥48፤ 1ጢሞ 1፥15
18፥14 ማቴ23፥12
18፥17 ማቴ11፥ 25፤ 18፥3

## የፈሪሳዊውና የቀረጥ ሰብሳቢው ምሳሌነት

[9]ራሳቸውን እንደ ጻድቃን በመቍጠር ለሚመኩና ሌሎቹን በንቀት ዐይን ለሚመለከቱ ሰዎች እንዲህ ሲል ይህን ምሳሌ ነገራቸው፤ [10]"ሁለት ሰዎች ሊጸልዩ ወደ ቤተ መቅደስ ወጡ፤ አንዱ ፈሪሳዊ፣ ሌላው ቀረጥ ሰብሳቢ ነበሩ። [11]ፈሪሳዊውም ቆሞ ስለ[²] ራሱ እንዲህ ይጸልይ ነበር፤ 'እግዚአብሔር ሆይ፤ እኔ እንደ ሌላው ሰው ሁሉ ቀማኛ፣ ዐመፀኛ፣ አመንዝራ፣ ይልቁንም እንደዚህ ቀረጥ ሰብሳቢ ባለመሆኔ አመሰግንሃለሁ፤ [12]በሳምንት ሁለት ጊዜ እጾማለሁ፤ ከማገኘውም ሁሉ ዐሥራት አወጣለሁ።'

[13]"ቀረጥ ሰብሳቢው ግን በርቀት ቆሞ፣ ወደ ሰማይ ቀና ብሎ ማየት እንኳ አልፈለገም፤ ነገር ግን ደረቱን እየደቃ፣ 'እግዚአብሔር ሆይ፤ እኔን ኀጢአተኛውን ማረኝ' ይል ነበር።

[14]"እላችኋለሁ፤ ከፈሪሳዊው ይልቅ ይኸኛው በእግዚአብሔር ዘንድ እንደ ጻድቅ ተቈጥሮ ወደ ቤቱ ተመለሰ፤ ራሱን ከፍ ከፍ የሚያደርግ ሁሉ ዝቅ ይላልና፤ ራሱን ዝቅ ዝቅ የሚያደርግ ግን ከፍ ይላል።"

## ኢየሱስ ከሕፃናት ጋር

18፥15-17 ተጓ ምብ – ማቴ 19፥13-15፤ ማር 10፥13-16

[15]ኢየሱስ እንዲዳስሳቸው ሰዎች ሕፃናትን ወደ እርሱ ያመጡ ነበር፤ ደቀ መዛሙርቱም ይህን ባዩ ጊዜ ገሠጿቸው። [16]ኢየሱስ ግን ሕፃናቱን ወደ ራሱ ጠርቶ እንዲህ አለ፤ "ሕፃናት ወደ እኔ እንዲመጡ ፍቀዱላቸው፤ አትከልክሏቸው፤ የእግዚአብሔር መንግሥት እንደነዚህ ላሉት ናትና። [17]እውነት እላችኋለሁ፤ የእግዚአብሔርን መንግሥት እንደ ሕፃን የማይቀበል ሁሉ ከቶ አይገባባትም።"

[¹]35 አንዳንድ ቅጆች ቍ 36 የላቸውም
[²]11 ወይም ለራሱ

17፥33 *ሕይወቱን አሳልፎ የሚሰጥ ግን ያቈያታል፤* የ9፥24 ማብ ይመ (ከማቴ 10፥39 ጋር ያነጻጽሩ)።

17፥35 *ትወሰዳለች፤* ምናልባት "ከጥፋት ስትድን" ወይም "ወደ መንግሥቱ ስትወሰድ" ማለት ሊሆን ይችላል። በዚህ ቍጥር ላይ በግልጽ የተጠቀሰው ግን፣ ሁለት ሰዎች በዚህ ዓለም ምንም ያህል ቢቀራረቡ፣ዘላለማዊ ፍጻሜያቸው ተመሳሳይ ሊሆን እንደማይችል ነው። አንዱ ወደ ፍርድና ወደ ጥፋት ሲሄድ፣ ሌላው ደግሞ ወደ ድነት፣ ሽልማትና በረከት ይሄዳል።

17፥37 *አሞሮች ይሰበሰባሉ፤* ምሳሌያዊ አነጋገር ነው፤ የማቴ 24፥28 ማብ ይመ። ደቀ መዛሙርቱ ላቀረቡት ጥያቄ ኢየሱስ የሰጠው መልስ፣ ይህ ክሥተት በሚመለከታቸው ሁሉ ዘንድ እውን እንደሚሆን ነው።

18፥2 *ሰውን የማያከብር፤* የሰው ችግር የማይገባው ወይም ይሉኝታ የሌለው ማለት ነው።

18፥3 *አንዲት መበለት፤* የሚረዳት ቤተ ሰብ ስለሌላት ምስኪንና ለችግር የተጋለጠች ናት፤ ተስፋ የምታደርገውም ፍትሕንና ጥሪቷን ብቻ ነበር።

18፥7 *እግዚአብሔርስ... አይፈርድላቸውምን?* መልካም ስም የሌለው፣ ስለ እውነተኛም ሆነ ስለ ሐሰተኞች ጒዳይ ደንታ የማይሰጠው ዐመፀኛ ዳኛ፣ ይህች ሴት ስለ ነዘነዘችው ብቻ ካደረገላት፣ ታዲያ እግዚአብሔር እንዴት ጸሎትን አይመልስም? *ከመጠን በላይ ችላ ይላቸዋልን?* እንደ ፈቃዱ ለሚመላለሱ ቅዱሳን እግዚአብሔር አይዘገይም። እንደ ዐመፀኛው ዳኛም እስኪሰለቸው ድረስ መነዝነዝ የለበትም።

18፥8 *እምነትን ያገኝ ይሆንን?* ይህ ዐይነት እምነት በጸሎትና በታማኝነት ጽኑ የሆነ ነው (ማቴ 24፥12-13 ይመ)፤ በተጨማሪም ኢየሱስ ዳግም መምጣቱን በድጋሚ ያስገነዘበ በትና መበለቲቱ ያሳየችውን ዐይነት ጽናት የሚያስፈልግበት መንፈሳዊ ድካምና የስደት ጊዜ እንደሚመጣ ያመለከተበት ነው።

18፥10 *ሊጸልዩ፤* ጸሎት የሚደረግባቸው ጊዜያት በየዕለቱ ጧትና ምሽት ከሚቀርበው መሥዋዕት ጋር ተያይዞ ይቀርባል፤ ሰዎችም ባመቻቸው ጊዜ ጸሎት ለማድረግ ወደ ቤተ መቅደስ ይሄዱ ነበር።

18፥12 *በሳምንት ሁለት ጊዜ እጾማለሁ፤* በማስተሰርያ ቀን ካልሆነ በቀር፣ መጾም በሙሴ ሕግ አልታዘዘም፤ ይሁን እንጂ ፈሪሳውያን ሰኞና ሐሙስ ይጾሙ ነበር (5፥33፤ማቴ 6፥16፤ 9፥14፤ ማር 2፥18፤ ሐሥ 27፥9 ይመ)። *ከማገኘውም ሁሉ ዐሥራት፤* ፈሪሳዊ በመሆኑ ዐሥራት ያወጣ የነበረው ከሚያገኘው ገንዘብ ብቻ ሳይሆን፣ ካለው ሀብት ጭምር ነበር።

18፥13 *እኔን ... ማረኝ፤* አስተስርይልኝ ማለት ነው (የ1ዮሐ2፥2 ማብ ይመ)። ይህ ቀረጥ ሰብሳቢ ኀጢአቱ ይቅር ይባልለት ዘንድ የተማመነው፣ በጎ ሥራውን ሳይሆን፣ የእግዚአብሔርን ምሕረት ነው።

18፥14 *በእግዚአብሔር ዘንድ እንደ ጻድቅ ተቈጥሮ፤* እግዚአብሔር አጸደቀው ኀጢአቱ ተሰርዮለት ጽድቅ የተቈጠረለት በራሱ ሥራ ሳይሆን (ቍ 9)፣ ከእግዚአብሔር ምሕረት የተነሣ ነው።

18፥17 *እንደ ሕፃን፤* በእምነት፣ ራስን በመስጠት፣ ግልጽ በመሆንና በፍጹም ቅንነት ማለት ነው (ማቴ 18፥3፤ 19፥14፤ ማር

### ሀብታሙ የአይሁድ አለቃ

18፥18-30 ተን ምብ - ማቴ-19፥16-29፤ ማር 10፥17-30

[18]ከአይሁድ አለቆች አንዱ፣ "ቸር መምህር ሆይ፤ የዘላለምን ሕይወት ለመውረስ ምን ላድርግ?" ሲል ጠየቀው።

[19]ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፤ "ስለ ምን ቸር ትለኛለህ? ከአንዱ ከእግዚአብሔር በቀር ቸር ማንም የለም፤ [20]'አታመንዝር፣ አትግደል፣ አትስረቅ፣ በሐሰት አትመስክር፣ አባትህንና እናትህን አክብር' የሚለውን ትእዛዝ ታውቃለህ።"

[21]ሰውየውም፣ "እነዚህንማ ከልጅነቴ ጀምሬ ጠብቄአለሁ" አለው።

[22]ኢየሱስም ይህን በሰማ ጊዜ፣ "እንግዲያውስ አንድ ነገር ይቀርሃል፤ ያለህን ሁሉ ሸጠህ ለድኾች ስጥ፤ በሰማይ መዝገብ ይኖርሃል፤ ከዚያም መጥተህ ተከተለኝ" አለው።

[23]ሰውየው ግን ይህን ሲሰማ፣ ብዙ ሀብት ስለ ነበረው በጣም ዐዘነ። [24]ኢየሱስም ሰውየውን ተመልክቶ እንዲህ አለ፤ "ብዙ ሀብት ላላቸው ወደ እግዚአብሔር መንግሥት መግባት እንዴት ጭንቅ ነው? [25]ሀብታም ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ከሚገባ ይልቅ ግመል በመርፌ ቀዳዳ ቢሾልክ ይቀላል።"

[26]ይህን የሰሙ ሰዎችም፣ "ታዲያ፣ ማን ሊድን ይችላል?" አሉ።

[27]ኢየሱስም፣ "በሰው ዘንድ የማይቻል በእግዚአብሔር ዘንድ ይቻላል" አለ።

[28]ጴጥሮስም፣ "እነሆ፤ እኛ ያለንን ሁሉ ትተን ተከትለንሃል" አለው።

[29]ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፤ "እውነት እላችኋለሁ፤ ስለ እግዚአብሔር መንግሥት ብሎ ቤቱን ወይም ሚስቱን ወይም ወንድሞቹን ወይም ወላጆቹን ወይም ልጆቹን የተወ፣ [30]በዚህ ዘመን ብዙ ዕጥፍ፣ በሚመጣውም ዘመን የዘላለምን ሕይወት የማይቀበል ማንም የለም።"

### ኢየሱስ ስለ ሞቱ ዳግመኛ ተናገረ

18፥31-33 ተን ምብ – ማቴ 20፥17-19፤ ማር 10፥32-34

[31]ኢየሱስም ዐሥራ ሁለቱን ደቀ መዛሙርት ለብቻ ወስዶ እንዲህ አላቸው፤ "እንግዲህ ወደ ኢየሩሳሌም ልንወጣ ነው፤ ነቢያት ስለ ሰው ልጅ የጻፉትም ሁሉ ይፈጸማል። [32]ለአሕዛብ አሳልፈው ይሰጡታል፤ እነርሱም ያፌዙበታል፤ ያንገላቱታል፤ ይተፉበታል፤ ይገርፉታል፤ ከዚያም ይገድሉታል። [33]እርሱም በሦስተኛው ቀን ከሙታን ይነሣል።"

[34]ደቀ መዛሙርቱ ግን ከዚህ ሁሉ የተረዱት አንድም ነገር አልነበረም፤ አባባሉም ተሰውሮባቸው ነበር፤ ስለ ምን እንደ ተናገረም አላወቁም።

### የዐይነ ስውሩ መፈወስ

18፥35-43 ተን ምብ – ማቴ 20፥29-34፤ ማር 10፥46-52

[35]ኢየሱስ ወደ ኢያሪኮ በቀረበ ጊዜ፣ አንድ ዐይነ ስውር መንገድ ዳር ተቀምጦ ይለምን ነበር። [36]ዐይነ ስውሩም ሕዝቡ በዚያ ሲያልፍ ሰምቶ ስለ ሁኔታው ጠየቃቸው። [37]እነርሱም፣ "የናዝሬቱ ኢየሱስ በዚህ እያለፈ ነው" ብለው ነገሩት።

[38]እርሱም፣ "የዳዊት ልጅ፣ ኢየሱስ ሆይ፤ ማረኝ!" እያለ ጮኸ።

[39]ከፊት የሚሄዱ ሰዎችም ዝም እንዲል ገሠጹት፤ እርሱ ግን፣ "የዳዊት ልጅ ሆይ፤ ማረኝ!" እያለ አብዝቶ ጮኸ።

[40]ኢየሱስም ቆም ብሎ ሰውየውን ወደ እርሱ እንዲያመጡት አዘዘ፤ ወደ እርሱም በቀረበ ጊዜ፣ [41]"ምን እንዳደርግልህ ትፈልጋለህ?" ብሎ ጠየቀው።

ዐይነ ስውሩም፣ "ጌታ ሆይ፤ ማየት እፈልጋለሁ" አለው።

[42]ኢየሱስም፣ "እይ፤ እምነትህ አድኖሃል" አለው። [43]ሰውየውም ወዲያውኑ ማየት ቻለ፤ እግዚአብሔርንም እያከበረ ኢየሱስን ተከተለው። ሕዝቡም ሁሉ ይህን ሲያዩ እግዚአብሔርን አመሰገኑ።

### ቀረጥ ሰብሳቢው ዘኬዎስ

**19** ኢየሱስ ወደ ኢያሪኮ ገብቶ በዚያ አልፎ ይሄድ ነበር። [2]ስሙ ዘኬዎስ የተባለ አንድ ሰው በዚያ ነበረ፤ ዋና ቀረጥ ሰብሳቢና ሀብታም ነበረ። [3]እርሱም ኢየሱስ የተባለው የትኛው እንደ ሆነ ሊያይ ይፈልግ ነበር፤ ቁመቱ አጭር ነበረና ከሕዝቡ ብዛት የተነሣ ሊያየው አልቻለም። [4]ኢየሱስ

18፥18 ሉቃ10፥25
18፥20 ዘፀ20፥12-16፤ ዘዳ5፥16-20፤ ሮሜ13፥9
18፥22 ማቴ19፥26፤ሐሥ2፥45
18፥24 ምሳ11፥28
18፥27 ማቴ19፥26
18፥28 ማቴ4፥19
18፥30 ማቴ12፥32፤ 25፥46
18፥31 መዝ22፤ ኢሳ 53፤ ማቴ8፥20፤ ሉቃ9፥51
18፥32 ማቴ16፥21፤ ሉቃ23፥1፤ሐሥ2፥23
18፥33 ማቴ16፥21
18፥34 ማር9፥32
18፥35 ሉቃ19፥1
18፥37 ሉቃ19፥4
18፥38 ቊ39፤ ማቴ9፥27፤17፥15፤ ሉቃ18፥13
18፥39 ቊ38
18፥42 ማቴ9፥22
18፥43 ማቴ9፥8፤ ሉቃ13፥17
19፥1 ሉቃ18፥35

---

10፥15 ይመ፤ ከጴጥ 2፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። የማር 10፥15 ማብ ይመ።

*18፥18-27፤* ይህን በተመለከተ የማር 10፥17-27 ማብ ይመ።

18፥18 *የዘላለምን ሕይወት፤* የማቴ 19፥16 ማብ ይመ።

18፥30 *በዚህ ዘመን... በሚመጣውም ዘመን፤* የአሁኑን የጎጢአትና የሥቃይ ዘመን፣ መሲሑ ሲመለስ የሚመጣውን መጪውን ዘመን ማለት ነው።

18፥31 *ነቢያት... የጻፉትም ሁሉ፤* ኢየሱስ ስለ ሞቱ አስቀድሞ የተናገረው ከሦስት ጊዜ በላይ ቢሆንም፣ ይኸኛው ሦስተኛ ነው ተብሎ ይታሰባል (የ17፥25 ማብ ይመ)፤ የመጀመሪያው በ9፥22 ላይ ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ በ9፥43-45 ላይ የተገለጸው ነው። የመሲሑ ሞት፣ ከምእተ ዓመታት በፊት አስቀድሞ ተነግሮ ነበር (ለምሳሌ መዝ 22፤ ኢሳ 53፤ ዘካ 13፥7፤ ሉቃ 24፥27፤ ማቴ 26፥24:31:54 ይመ)። *የሰው ልጅ፤* የማር 8፥31 ማብ ይመ።

18፥35 *ወደ ኢያሪኮ በቀረበ ጊዜ፤* የማር 10፥46 ማብ ይመ። *አንድ ዐይነ ስውር፤* በርጤሜዎስ ነው (ማር 10፥46)። ማቴዎስ፣ ሁለት ዐይነ ስውራን እንደ ተፈወሱ ጽፎአል (የማቴ 8፥28 ማብ ይመ)። ምናልባት ማርቆስና ሉቃስ የሁለተኛውን መገኘት ያልጻፉት፣ ከሁለት አንዱ አፈ ቀላጤና ላቅ ብሎ የታየ በመሆኑ ሳይሆን አይቀርም።

18፥38-39 *የዳዊት ልጅ፤* የመሲሑ ማዕረግ ነው (ማቴ 22፥41-45፤ ማር 12፥35፤ ዮሐ 7፥42 ይመ፤ እንዲሁም 2ሳሙ 7፥12-13፤ መዝ 89፥3-4፤ አሞ 9፥11፤ ማቴ 12፥23፤ 21፥15-16 ይመ)።

18፥42 *እምነትህ፤* የ17፥19 ማብ ይመ።

19፥1 *ወደ ኢያሪኮ ገብቶ፤* የማር 10፥46 ማብ ይመ።

19፥2 *ዋና ቀረጥ ሰብሳቢና፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ይህ ማዕረግ ተጽፎ የሚገኘው፣ በዚህ ቦታ ብቻ ነው፤ ምናልባት በእርሱ ሥር ሌሎች የአንድ አውራጃ ቀረጥ ሰብሳቢዎች ያሉት ሹም ሊሆን ይችላል፤ በዚህ ወቅት ይህ አውራጃ ሀብታሞች ያሉበት ስለሆነ፤ ዘኬዎስ ሀብታም ሆኖ መገኘቱ የሚያስደንቅ አይደለም፤ የ3፥12፤ ማር 2፥14-15 ማብ ይመ።

በዚያ መንገድ ያልፍ ስለ ነበርም፣ ወደ ፊት ሮጦ አንድ ሾላ ዛፍ ላይ ወጣ::

5ኢየሱስም እዚያ ቦታ ሲደርስ፣ ቀና ብሎ፣ “ዘኬዎስ ሆይ፤ ዛሬ አንተ ቤት መዋል ይገባኛልና ፈጥነህ ውረድ” አለው:: 6እርሱም ፈጥኖ ወርዶ በደስታ ተቀበለው::

7በዚያ የነበሩ ሰዎችም ይህንን አይተው፣ “ከኀጢአተኛ ቤት ገብቶ ሊስተናገድ ነው::” በማለት ሁሉም ማጒረምረም ጀመሩ::

8ዘኬዎስ ግን ቆመና ጌታን፣ “ጌታ ሆይ፤ እነሆ ካለኝ ሀብት ሁሉ ግማሹን ለድኾች እሰጣለሁ፤ ማንንም በሐሰት ቀምቼ ከሆነ፣ አራት ዕጥፍ አድርጌ እመልሳለሁ” አለው::

9ኢየሱስም እንዲህ አለው፤ “ይህ ሰው ደግሞ የአብርሃም ልጅ ስለ ሆነ፣ ዛሬ መዳን ወደዚህ ቤት መጥቶአል፤

10ምክንያቱም የሰው ልጅ የመጣው የጠፋውን ሊፈልግና ሊያድን ነው::”

## የዐሥሩ ምናን ምሳሌ

19፥12-27 ማመ – ማቴ 25፥14-30

11ሕዝቡ ይህን እየሰሙ ሳሉ፣ በምሳሌ መናገሩን ቀጠለ፤ ምክንያቱም ወደ ኢየሩሳሌም በመቃረቡና ሰዎቹም የእግዚአብሔር መንግሥት የሚገለጥ ስለ መሰላቸው ነው:: 12ስለዚህም እንዲህ አለ፤ “አንድ መስፍን የንጉሥነትን ማዕረግ ተቀብሎ ለመመለስ ወደ ሩቅ አገር ሄደ:: 13ከአገልጋዮቹም መካከል ዐሥሩን ጠርቶ ዐሥር ምናን ሰጣቸውና “ተመልሼ እስክመጣ ድረስ በዚህ ገንዘብ ነግዱበት” አላቸው::

14“የአገሩ ሰዎች ግን ስለ ጠሉት፣ ‘ይህ ሰው በላያችን እንዲነግሥ አንፈልግም’ ብለው ከኋላው መልእክተኞችን ላኩበት::

15“ይሁን እንጂ ይህ መስፍን ንጉሥ ሆኖ ወደ አገሩ ተመለሰ፤ እነዚያ አገልጋዮቹም እርሱ በሰጣቸው ገንዘብ ነግደው ምን ያህል እንዳተረፉ ለማወቅ አስጠራቸው::

16“የመጀመሪያው አገልጋይ ቀርቦ፣ ‘ጌታ ሆይ፤ የሰጠኸኝ ምናን ዐሥር ምናን ትርፍ አስገኝቶአል’ አለው::

17“ጌታውም፣ ‘አንተ ታማኝ አገልጋይ፣ መልካም አድርገሃል፤ በትንሽ ነገር ታማኝ ሆነህ ስለ ተገኘህ፣ በዐሥር ከተሞች ላይ ሥልጣን ተሰጥቶሃል’ አለው::

18“ሁለተኛውም ቀርቦ፣ ‘ጌታ ሆይ፤ የሰጠኸኝ ምናን አምስት ምናን ትርፍ አስገኝቶአል’ አለው::

19“ጌታውም፣ ‘አንተ ደግሞ በአምስት ከተሞች ላይ ሥልጣን ተሰጥቶሃል’ አለው::

20“ሌላውም አገልጋይ ቀርቦ እንዲህ አለው፤ ‘ጌታ ሆይ፤ በጨርቅ ጠቅልዬ ያቈየሁት ምናንህ ይኸው፤ 21አንተ ያላስቀመጥኸውን የምትወስድ፣ ያልዘራኸውን የምታጭድ ጨካኝ ሰው ስለ ሆንህ ፈራሁህ::’

22“ጌታውም እንዲህ አለው፤ ‘አንተ ክፉ አገልጋይ! በራስህ ቃል እፈርድብሃለሁ፤ ያላስቀመጥሁትን የምወስድ፣ ያልዘራሁትን የማጭድ፣ ጨካኝ ሰው መሆኔን ካወቅህ፣ 23መጥቼ ገንዘቤን ከነትርፉ እንድወስድ፣ ለምን ለሚሠሩበት ሰዎች አልሰጠህም?’

24“ጌታውም እዚያ የቆሙትን፣ ‘ምናኑን ውሰዱበትና ዐሥር ምናን ላለው ስጡት’ አላቸው::

25“እነርሱም፣ ‘ጌታ ሆይ፤ እርሱ እኮ ዐሥር ምናን አለው’ አሉት::

26“እርሱም እንዲህ አለ፤ ‘እላችኋለሁ፤ ላለው ሁሉ ይጨመርለታል፤ የሌለው ግን ያው ያለው እንኳ ይወሰድበታል:: 27ነገር ግን እኔ በላያቸው እንዳልነግሥ የፈለጉትን እነዚያን ጠላቶቼን ወደዚህ አምጡና በፊቴ ዕረዷቸው::’ ”

19፥4 1ነገ10፥27፤ 1ዜና27፥28፤ ኢሳ 9፥10፤ሉቃ18፥37
19፥7 ማቴ9፥11
19፥8 ዘፀ22፥1፤ ዘሌ 6፥4:5፤ ዘኍ5፥7፤ 2ሳሙ12፥6፤ ሕዝ 33፥14:15፤ ሉቃ3፥12:13
19፥9 ሉቃ3፥8
19፥10 ሕዝ34፥12:16፤ዮሐ3፥17
19፥11 ማቴ3፥2፤ ሉቃ17፥20፤ ሐሥ1፥6
19፥13 ማር13፥34
19፥17 ምሳ27፥18፤ ሉቃ6፥10
19፥21 ማቴ25፥24
19፥22 2ሳሙ1፥16፤ኢዮ15፥6፤ ማቴ25፥26
19፥26 ማቴ25፥29

19፥4 *ሾላ ዛፍ፤* ከ9 እስከ 10 ሜትር የሚረዝም ወፍራም ግንድና የተንሰራፋ ቅርንጫፍ ያለው ሲሆን፣ ትልቅ ሰውን መሸከም የሚችል ጠንካራ ዛፍ ነው::

19፥5 *አንተ ቤት መዋል ይገባኛልና፤* መለኮታዊ ቸርነት ያመለክታል::

19፥8 *አራት ዕጥፍ፤* የሰረቀ ሰው ካሳ እንዲከፍል ሕጉ ከደነገገው በላይ ከፍተኛ ክፍያ ነው፤ (ዘፀ 22፥1፤2ሳሙ 12፥6፤ ከምሳ 6፥31 ጋር ያነጻጽሩ)::

19፥9 *የአብርሃም ልጅ፤* እውነተኛ አይሁድ ማለት ነው፤ ይኸውም በዘር ግንድ ብቻ ሳይሆን፣ የአብርሃምን እምነት (ሮሜ 4፥12) አርአያ አድርጎ የተቀበለ ሰው ማለት ነው:: የአይሁድ ኅብረተሰብ ይህን ቀረጥ ሰብሳቢ ቢያገለውም፣ ኢየሱስ ይህን ሰው የተመለከተው በርኅራኄ ነበር::

*19፥10፤* በሉቃስ ወንጌል ውስጥ ቍልፍ ቍጥር ነው፤ *የሰው ልጅ፤* የመሲሑ የማዕረግ ስም ሲሆን (ዳን 7፥13)፣ ይህም በአራቱ ወንጌላት ውስጥ ኢየሱስ በሐሥ 7፥56 እስጢፋኖስ፣ እንዲሁም በራእ 1፥13 ዮሐንስ ተጠቅመውበታል:: በመግቢያው ላይ ‘አደረጃጀት’ የሚለውንና የማር 8፥31 ማብ ይመ:: *ሊፈልግና ሊያድን፤* ኢየሱስ ድነትን ለመስጠት (18፥18)፣ እንዲሁም የእግዚአብሔርን መንግሥት ለሰዎች ለመግለጥ የመጣበትን (18፥25) ዐላማ አጠቃሎ የያዘ ሐሳብ ነው፤ የ15፥32 ማብ ይመ::

19፥11 *የእግዚአብሔር መንግሥት የሚገለጥ፤* መሲሑ በኀይልና በክብር መጥቶ፣ ፖለቲካዊና ወታደራዊ ጠላቶቻቸውን በማሸነፍ ምድራዊ መንግሥቱን እንደሚያቋቁም ይጠብቁ ነበር::

19፥12 *የንጉሥነትን ማዕረግ ተቀብሎ፤* ይህ የተለመደ አሠራር ባይሆንም፣ ሄሮድሳውያን አይሁዳውያንን ለመግዛት ወደ ሮም በመሄድ፣ ገዥ በመሆን በዚሁ መልክ መጥተዋል፤ ልክ እንደዚህ ኢየሱስም ወደ አባቱ ከሄደ በኋላ፣ ወደ ፊት ንጉሥ ሆኖ ይመጣል፤ ተመልሶ እስከሚመጣም ድረስ፣ አገልጋዮቹ የጌታቸውን ሥራ እንዲያከናውኑ ኀላፊነት ተጥሎባቸዋል (ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነውን ምሳሌ በማቴ 25፥14-30 ላይ ይመ)::

19፥13 *ዐሥር ምናን፤* የአንድ ሠራተኛ ከሁለት እስከ ሦስት ዓመት ደመወዝ የሚያህል ገንዘብ ነው፤ በማቴዎስ ወንጌል ላይ ከተሰጠው ምሳሌ ጋር ሲነጻጸር፣ይህኛው አነስተኛ ነው፤ እዚህ ላይ ለዐሥሩ ሠራተኞች የተሰጠው የገንዘብ መጠንም እኩል ነው::

19፥14 *መልእክተኞችን ላኩበት፤* የሴፍ ወልደ ኮሪዮን፣ የዚህ ዐይነት ሁኔታ ከ30 ዓመታት በፊት በአርኬላዎስ ላይ እንደ ደረሰ ጽፎአል፤ ይህ ታሪክ በዚህ ሁኔታ የተነገረው፣ አይሁዳውያን የኢየሱስን ንጉሥነት አንቀበልም እንዳይሉ ለማስጠንቀቅ ነው::

19፥22 *ጨካኝ ሰው መሆኔን ካወቅህ፤* ጌታው የአገልጋዩን ንግግር ትክክል ነው ብሎ አልተቀበለም፤ ይሁን እንጂ ለአገልጋዩ መልሶ በጥያቄ መልክ አቀረበለት፤ አገልጋዩም ያወቀውን ይህን ነገር ማድረግ ነበረበት::

19፥26 *ይጨመርለታል ... ያው ያለው እንኳ ይወሰድበታል፤* 8፥18፤ 17፥33፤ ማቴ 13፥12 ይመ:: ለራሳቸውና ለሌሎች የወንጌልን መንፈሳዊ በረከት የሚፈልጉ፣ ይበልጥ ይባረካሉ፤ የተቀበሉትን የሚንቁ ወይም የሚያባክኑ ግን ያላቸውን እንኳ በማጣት በመንፈስ ይደኸያሉ::

19፥27 *እነዚያን ጠላቶቼን ... ዕረዷቸው፤* በ70 ዓ.ም

## ኢየሱስ በታላቅ ክብር ወደ ኢየሩሳሌም መግባቱ

19፥29-38 ተጓ ምብ – ማቴ 21፥1-9፤ ማር 11፥1-10
19፥35-38 ተጓ ምብ – ዮሐ 12፥12-15

[28]ኢየሱስ ይህን ከተናገረ በኋላ፣ ወደ ኢየሩሳሌም ሊወጣ ቀድሞአቸው ይሄድ ነበር። [29]ደብረ ዘይት በተባለው ተራራ ወደሚገኙት፣ ወደ ቤተ ፋጌና ወደ ቢታንያ ከተሞች በቀረበ ጊዜ፣ ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን እንዲህ ሲል ላካቸው፤ [30]"በፊታችሁ ወዳለችው መንደር ሂዱ፤ ወደዚያም ስትገቡ ማንም ገና ያልተቀመጠበት ውርንጫ ታስሮ ታገኛላችሁ፤ ፈትታችሁ ወደዚህ አምጡት። [31]ማንም፣ 'ለምን ትፈቱታላችሁ?' ብሎ ቢጠይቃችሁ፣ 'ለጌታ ያስፈልገዋል' በሉት።"

[32]የተላኩትም ሄደው ልክ እንደ ነገራቸው ሆኖ አገኙት። [33]ባለቤቶቹም ውርንጫውን ሲፈቱ አይተው፣ "ውርንጫውን ለምን ትፈታላችሁ?" አሏቸው።

[34]እነርሱም፣ "ለጌታ ያስፈልገዋል" አሉ።

[35]ከዚያም ውርንጫውን ወደ ኢየሱስ አመጡት፤ ልብሳቸውንም በላዩ ጣል አድርገው ኢየሱስን በውርንጫው ላይ አስቀመጡት። [36]ሰዎችም እርሱ በሚሄድበት መንገድ ላይ ልብሳቸውን ያነጥፉ ነበር።

[37]በደብረ ዘይት ተራራ ቍልቍል ወደ ሚወስደው መንገድ በተቃረበ ጊዜ፣ ቍጥራቸው እጅግ ብዙ የሆነ ደቀ መዛሙርት ስላዩት ታምራት ሁሉ ደስ እያላቸው ድምፃቸውን ከፍ በማድረግ እንዲህ እያሉ እግዚአብሔርን ያመሰግኑ ጀመር፤

[38]"በጌታ ስም የሚመጣው ንጉሥ የተባረከ ነው!"

"በሰማይ ሰላም፣ በአርያምም ክብር ይሁን!"

[39]በሕዝቡ መካከል የነበሩ አንዳንድ ፈሪሳውያንም ኢየሱስን፣ "መምህር ሆይ፤ ደቀ መዛሙርትህን ገሥጻቸው እንጂ" አሉት።

[40]እርሱም፣ እላችኋለሁ፤ "እነርሱ ዝም ቢሉ፣ ድንጋዮች ይጮኻሉ" አላቸው።

[41]ኢየሱስም ወደ ኢየሩሳሌም ሲቃረብ ከተማዋን አይቶ አለቀሰላት፤ [42]እንዲህም አለ፤ "ሰላምሽ የሚሆነውን ምነው አንቺ ዛሬ በተረዳሽ ኖሮ! አሁን ግን ከዐይንሽ ተሰውሮአል፤ [43]ጠላቶችሽ ዙሪያሽን ቅጥር ሠርተው፣ ከየአቅጣጫውም ከበው አንቺን የሚያስጨንቁበት ጊዜ ይመጣልና፤ [44]አንቺንና በቅጥርሽ ውስጥ የሚኖሩትንም ልጆችሽን ከዐፈር ይደባልቃሉ፤ ድንጋይም በድንጋይ ላይ አይተዉም፤ የመጐብኛሽን ጊዜ አላወቅሽምና።"

19፥28 ማር10፥32፤ሉቃ9፥51
19፥29 ማቴ21፥1፤ 21፥17
19፥32 ሉቃ22፥13
19፥36 2ነገ9፥13
19፥37 ማቴ21፥1
19፥38 መዝ118፥26፤ ሉቃ2፥14፤ 13፥35
19፥39 ማቴ 21፥15:16
19፥40 ዕን2፥11
19፥41 ኢሳ22፥4፤ ሉቃ13፥34:35
19፥43 ኢሳ29፥3፤ ኤር6፥6፤ ሕዝ 4፥2፤ 26፥8፤ ሉቃ21፥20
19፥44 መዝ137፥9፤ ሉቃ21፥6፤ 1ጴጥ2፥12
19፥46 ኢሳ56፥7፤ ኤር7፥11
19፥47 ማቴ12፥14፤ 26፥55፤ ማር11፥18

## ኢየሱስ በቤተ መቅደስ

19፥45-46 ተጓ ምብ – ማቴ 21፥12-16፤ ማር 11፥15-18፤ ዮሐ 2፥13-16

[45]ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ወደ ቤተ መቅደስ ገብቶ፣ ሻጮችን ከዚያ አስወጣ፤ [46]ደግሞም "'ቤቴ የጸሎት ቤት ይሆናል' ተብሎ ተጽፎአል፤ እናንተ ግን 'የወንበዴዎች ዋሻ' አደረጋችሁት" አላቸው።

[47]በየቀኑም በቤተ መቅደስ ያስተምር ነበር፤ የካህናት አለቆች፣ ጸሐፍትና የሕዝብ መሪዎችም ሊገድሉት ይፈልጉ ነበር፤ [48]ነገር ግን ሕዝቡ ሁሉ ከእርሱ ጋር ተቈራኝተው ትምህርቱን ይከታተሉ ስለ ነበር፣ የሚያደርጉት ግራ ገባቸው።

---

የሆነውን የኢየሩሳሌምን ጥፋት የሚመለከት ሳይሆን አይቀርም። በንጉሡ ላይ ዐምፀው በብርቱ የተቃወሙት (ቍ 14) የሚቀጡት ቅጣት፣ ዐደራውን ችላ ካለው አገልጋይ በላይ እጅግ የከፋ ነው።

*19፥28-44፤* ኢየሱስ በታላቅ ክብር ወደ ኢየሩሳሌም የገባው፣ በሕማማቱ ሰሞን እሁድ ቀን ነበር። "የክርስቶስ ምድራዊ ሕይወት" እና "የሕማማቱ ሳምንት" የሚለውን ይመ።

19፥29 *ደብረ ዘይት... ተራራ፤* ከሰሜን ወደ ደቡብ አንድ ኪሎ ሜትር ያህል ርዝመት ያለውና የኢየሩሳሌምን ምሥራቃዊ ክፍል የሚሸፍን ተራራ ነው፤ በኢየሩሳሌምና በተራራው መካከል የቄድሮን ሸለቆ ይገኛል (የዘካ 14፥4፤ ማር 11፥1 ማብ ይመ)። *ቤተ ፋጌ፤* ከኢያሪኮ ወደ ኢየሩሳሌም በሚወስደው መንገድ ላይ የምትገኝ መንደር ናት። *ቢታንያ፤* ከኢየሩሳሌም በስተ ደቡብ ምሥራቅ 3ኪ.ሜ ያህል ርቃ የምትገኝ ስትሆን (ዮሐ 11፥18)፤ ይህችም የማርያም፣ የማርታና የአልዓዛር መኖሪያ መንደር ናት። *ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን፤* በዚህም ሆነ በሌሎች ተመሳሳይ ምንባቦች ስማቸው አልተጠቀሰም (ማቴ 21፥1፤ ማር 11፥1፤ ይመ ከዮሐ 12፥14 ጋር ያነጻጽሩ)።

19፥30 *መንደር፤* ምናልባት ቤተ ፋጌ ልትሆን ትችላለች። *ማንም... ያልተቀመጠበት፤* ለምንም ዐይነት አገልግሎት ያልዋለ ማለት ነው (ዘኍ19፥2 ፤ 1ሳሙ6፥7)። *ውርንጫ፤* በሌሎች ትረካዎች ውስጥም የአህያ ውርንጫ ተብሎ በግልጽ የተጠቀሰ ሲሆን (ዮሐ 12፥15)፣ የውርንጫው እናትም (ማቴ 21፥7) ከእርሱ ጋር ነበረች። እዚህ ላይ ሉቃስ የተጠቀመው የሰብዓ ሊቃናት ተርጓሚዎች "አህያ" የሚለውን የዕብራይስጥ ቃል ወደ ግሪክ ቋንቋ ሲመልሱ የተጠቀሙበትን ነው። በዚህ ጊዜ ኢየሱስ በአህያ ላይ ተቀምጦ ወደ ኢየሩሳሌም ለመግባት የፈለገው፣ በዳዊት ዙፋን እንደ ሚቀመጥ (ዘካ 9፥9) ነቢያት የተነበዩለት የዳዊት ልጅ እርሱ መሆኑን በይፋ ለማሳየት ነው (1ነገ 1፥33:44)።

19፥31 *ለጌታ፤* እግዚአብሔርን፣ በይበልጥም ኢየሱስን የሚ ያመለክት ሲሆን፣ የእስራኤል ብቸኛ ጌታም እርሱ መሆኑን ያሳ ወቀበት ነው።

19፥37 *ታምራት ሁሉ፤* የአልዓዛር ከሞት መነሣትና የዐይነ ስውሩ የበርጠሜዎስ መፈወስ በምሳሌነት የሚጠቀሱ የቅርብ ትዝታዎች ሲሆን፣ በዮሐንስ ወንጌል ውስጥ የሚገኙት ኢየሱስ በልዩ ልዩ ጊዜያት በኢየሩሳሌም ያከናወናቸውና በገሊላ የሰጠው ጠቅላላ አገልግሎቱንም ያካትታል (ከማቴ 21፥14፤ ዮሐ 12፥17 ጋር ያነጻጽሩ)።

19፥43 *ጠላቶችሽ ዙሪያሽን ቅጥር ሠርተው፤* 21፥20 ይመ፤ ሮማውያን በ70 ዓ.ም. ኢየሩሳሌምን በወረሩና በከተማዋ ዙሪያ ቅጥር በሠሩ ጊዜ ይህ ትንቢት ተፈጽሞአል፤ በተጨማሪም በብሉይ ኪዳን የተነገሩን ትንቢቶች የሚያስታውስ ነው (ኢሳ 29፥3፤ 37፥33፤ ሕዝ 4፥1-3)።

19፥44 *የመጐብኛሽን ጊዜ፤* በመሢሑ በኢየሱስ በኩል እግዚአብሔር ራሱን ለአይሁድ ቢገልጥም፣ እነርሱ ግን ስላላስተዋሉት አልተቀበሉትም (ዮሐ 1፥10-11፤ ይመ፤ ከሉቃ 20፥13-16 ጋር ያነጻጽሩ)።

*19፥45፤* ማርቆስ (11፥11-17)፣ ኢየሱስ ቤተ መቅደሱን ያነጻው በታላቅ ክብር ወደ ኢየሩሳሌም በገባ ማግስትና በሰሞነ ሕማማቱ ሰኞ ቀን እንደ ሆነ ገለጸአል። *ቤተ መቅደስ፤* ለመሥዋዕት የሚሆኑ እንስሳት ከልክ በላይ በሆነ ዋጋ የሚሸጡበትና አሕዛብ የሚቀመጡበት የቤተ መቅደሱ የውጪ አደባባይ ነው። ቤተ መቅደሱን ያነጻው አገልግሎቱን በጀመረ ጊዜ እንደ ሆነ ዮሐንስ ሲገልጽ (ዮሐ 2፥13-25)፣ ተመሳሳይ ወንጌላት ግን (ማቴ 21፥12-13፤ ማር 11፥15-17) በአገልግሎቱ መደምደሚያ ላይ መሆኑን ይገልጻሉ (የማቴ 21፥12-17፤ ዮሐ 2፥14-17 ማብ ይመ)።

19፥47 *የካህናት አለቆች፤* 3፥2፤22፥52፤ 23፥4፤ 24፥20 ይመ፤ የአይሁድ ሕዝብ የአስተዳደር ሸንጎ አባላት ናቸው (የማር 14፥55 ማብ ይመ)። *ሊገድሉት ይፈልጉ ነበር፤* ሉቃ 20፥19-20 ይመ (ከዮሐ 7፥1፤ 11፥53-57 ጋር ያነጻጽሩ)።

## የኢየሱስ ሥልጣን ለአይሁድ አጠያያቂ ሆነባቸው

20፥1-8 ተን ምብ-ማቴ 21፥23-27፤ማር 11፥27-33

**20** አንድ ቀን ኢየሱስ ሕዝቡን በቤተ መቅደስ ሲያስተምርና ወንጌልን ሲሰብክ የካህናት አለቆች፣ ጸሐፍትና ሽማግሌዎች ተሰብስበው ወደ እርሱ መጡ፤ [2]እነርሱም፣ "እነዚህን ነገሮች የምታደርገው በምን ሥልጣን እንደ ሆነ ንገረን፤ ሥልጣንስ የሰጠህ ለመሆኑ እርሱ ማን ነው?" ብለው ጠየቁት።

[3]እርሱም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "እኔም አንድ ጥያቄ ልጠይቃችሁ፤ እስቲ መልሱልኝ፤ [4]የዮሐንስ ጥምቀት ከሰማይ ነበር ወይስ ከሰው?"

[5]እነርሱም እንዲህ ብለው እርስ በርስ ተመካከሩ፤ " 'ከሰማይ' ብንል፣ 'ታዲያ፣ ለምን አላመናችሁበትም?' ይለናል፤ [6]'ከሰው' ብንል ሕዝቡ ሁሉ ዮሐንስ ነቢይ መሆኑን ስለሚያምኑ በድንጋይ ይወግሩናል።"

[7]ስለዚህ፣ "ከየት እንደ ሆነ አናውቅም" ብለው መለሱለት።

[8]ኢየሱስም፣ "እንግዲያውስ እኔም እነዚህን ነገሮች በምን ሥልጣን እንደማደርግ አልነግራችሁም" አላቸው።

## የጭሰኞቹ ምሳሌ

20፥9-19 ተን ምብ –ማቴ 21፥33-46፤ ማር 12፥1-12

[9]ከዚህ በኋላ ኢየሱስ እንዲህ ሲል ይህን ምሳሌ ለሕዝቡ ይነግራቸው ጀመር፤ "አንድ ሰው የወይን ተክል ተከለ፤ ለገበሬዎችም አከራየና ወደ ሌላ አገር ሄዶ ብዙ ጊዜ ቈየ። [10]በመከርም ወራት፣ ከወይኑ ፍሬ እንዲልኩለት አገልጋዩን ወደ እነዚህ ገበሬዎች ላከ፤ ገበሬዎቹ ግን አገልጋዩን ደብድበው ባዶ እጁን ሰደዱት። [11]ቀጥሎም ሌላ አገልጋዩን ላከ፤ ገበሬዎቹም እርሱንም ደግሞ ደበደቡት፤ አዋርደውም ባዶ እጁን ሰደዱት። [12]አሁንም ቀጥሎ ሦስተኛ አገልጋዩን ላከ፤ ገበሬዎቹም እርሱንም ደግሞ አቍስለው ወደ ውጭ ጣሉት።

[13]"የወይኑ ተክል ባለቤትም፣ 'እንግዲህ ምን ላድርግ? እስቲ ደግሞ የምወደውን ልጄን እልካለሁ፤ ምናልባት እርሱን ያከብሩት ይሆናል' አለ።

[14]"ገበሬዎቹ ግን ልጁን ባዩት ጊዜ፣ ይህ እኮ ወራሹ ነው፣ ኑና እንግደለው፤ በዚህም ርስቱ የእኛ ይሆናል" እየተባባሉ ተመካከሩ፤ [15]ከወይኑም ተክል ቦታ ወደ ውጭ አውጥተው ገደሉት።

"እንግዲህ የወይኑ ተክል ባለቤት ምን ያደርጋቸዋል? [16]መጥቶ እነዚያን ገበሬዎች ያጠፋቸዋል፤ የወይኑንም ተክል ቦታ ለሌሎች ይሰጣል።"

ሕዝቡም ይህን በሰሙ ጊዜ፣ 'እንዲህ ያለውንስ አያምጣው' አሉ።

[17]ኢየሱስም ወደ እነርሱ ተመልክቶ እንዲህ አላቸው፤

" 'ታዲያ ግንበኞች የናቁት ድንጋይ፣
እርሱ የማእዘን ራስ[a] ሆነ' ተብሎ
የተጻፈው ትርጕሙ ምንድን ነው?

[18]በዚህ ድንጋይ ላይ የሚወድቅ ሁሉ ይቀጠቀጣል፤ ድንጋዩም በላዩ የሚወድቅበት ሁሉ ይደቃል።"

[19]ጸሐፍትና የካህናት አለቆችም ይህንን ምሳሌ የተናገረው በእነርሱ ላይ መሆኑን ስላወቁ፣ በዚያኑ ሰዓት ሊይዙት ፈልገው ነበር፤ ነገር ግን ሕዝቡን ፈሩ።

## ለቄሣር ግብር መክፈል

20፥20-26 ተን ምብ – ማቴ 22፥15-22፤ ማር 12፥13-17

[20]ኢየሱስን አሳልፈው ለገዥው ኀይልና ሥልጣን ለመስጠት፣ ከአፉ በሚወጣ ቃል

[a]17 ወይም የማእዘን ድንጋይ

20፥1 ማቴ26፥55፤ ሉቃ8፥1
20፥2 ዮሐ2፥18፤ ሐሥ4፥7፤ 7፥27
20፥4 ማር1፥4
20፥6 ማቴ11፥9፤ ሉቃ7፥29
20፥9 ኢሳ5፥1-7፤ ማቴ25፥14
20፥13 ማቴ3፥17
20፥16 ሉቃ19፥27
20፥17 መዝ 118፥22፤ሐሥ 4፥11
20፥18 ኢሳ8፥14፥15
20፥19 ማር11፥18፤ ሉቃ19፥47
20፥20 ማቴ12፥10፤27፥2

*20፥1* በ20፥1-21፥36 ላይ የተመለከቱት ሁኔታዎች ሁሉ የተከናወኑት በሰሞነ ሕማማት ሳምንት ማክሰኞ ቀን ነው፤ ይህም ረጅም ክርክር የተካሄደበት ቀን ነበር። *አንድ ቀን፣* ቀኑ ተለይቶ ባይገለጽም፣ በማርቆስ ወንጌል ግን (ማር 11፥19-20፡ 27-33)፣ ይህ ቀን (ማክሰኞ) ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም በክብር ከገባና (እሁድ) ቤተ መቅደሱን ካነጻ በኋላ (ሰኞ) የሚገኘው ነው። *የካህናት አለቆች፣* 19፥47፤ ይመ፤ የማቴ 2፥4 ማብ ይመ። *ጸሐፍት፣* 5፥30፤ ይመ የ5፥17፤ ማቴ 2፥4 ማብ ይመ። *ሽማግሌዎች፣* የማቴ 15፥2 ማብ ይመ። እነዚህ ሁሉ የአይሁድ ሕዝብ የአስተዳደር ጉባኤ በሆነው ሸንጎ ውስጥ ተወክለዋል (22፥66 ይመ)።

20፥2 *ሥልጣንስ የሰጠህ... ማን ነው?* ይህን ጥያቄ ለመጥምቁ ዮሐንስና (ዮሐ 1፥19-25) ኢየሱስ ክርስቶስ አገልግሎቱን በጀመረ ጊዜም አቅርበው ነበር (ዮሐ 2፥18-22)። ጥያቄአቸው ያተኰረው በቤተ መቅደሱ መንጻት ላይ ቢሆንም፣ ከጠያቂዎቹ ሥልጣንና ከገንዘብ ጥቅማቸው ጋርም የተያያዘ ነበር፤ ይህን ጥያቄ ያቀረቡበት ዐላማ፣ ኢየሱስ በሕዝብ ዘንድ ተቀባይነት እንዲያጣ ወይም የሮም ባለሥልጣናት በክፉ ዐይን እንዲያዩት አስበው ሳይሆን አይቀርም።

20፥4 *የዮሐንስ ጥምቀት ከሰማይ ... ወይስ ከሰው?* ኢየሱስ ለቀረበለት ጥያቄ መልስ ለመስጠት፣ የዮሐንስ አገልግሎት ከእግዚአብሔር ነበር ወይስ ከራሱ? የሚሉትን ሁለት አማራጮች በጥያቄ መልክ በማቅረብ/ጥያቄያቸውን በጥያቄ መለሰ፤ እነርሱም የቀ ረበላቸውን ጥያቄ ለመመለስ ፈቃደኞች ባለመሆናቸው ራሳቸውን አጕል ሁኔታ ውስጥ ከተቱ። *ከሰማይ፣* የማር 11፥30 ማብ ይመ።

20፥10 *ከወይኑ ፍሬ እንዲልኩለት፣* በስምምነታቸው መሠረት፣ የመሬቱ ባለቤት የተወሰነ ድርሻ ማግኘት ይገባው ስለ ነበር፣ ወቅቱ ሲደርስ ድርሻውን ለመቀበል ይጠብቅ ነበር። *አገልጋዩን ... ላከ፣* ይህ ምሳሌ (ቍ9)፣ በኢሳ 5፥1-7 ያለውን የሚያስታውስ ነው። ወደ ገበሬዎቹ ተልከው የነበሩት አገልጋዮች፣ እግዚአብሔር በጥንት ዘመን የላካቸውንና የእስራኤልም ሕዝብ የተቃወማቸውን ነቢያት ይወክላሉ (ነህ 9፥26፤ ኤር 7፥25-26፤ 25፥4-7፤ ማቴ23፥ 34፤ ሐሥ 7፥52፤ ዕብ 11፥36-38 ይመ)።

20፥13 *የምወደውን ልጄን፣* ስለ ተወዳጁ ልጅ መጠቀሱ፣ የአብ የባሕርዩ ልጅ የሆነውን ጌታችንን ኢየሱስ ክርስቶስን ለማመልከት ነው (3፥22፤ ማቴ 17፥5 ይመ)።

20፥14 *ርስቱ የእኛ ይሆናል፣* የማር 12፥7 ማብ ይመ።

20፥16 *የወይኑንም ተክል ቦታ ለሌሎች ይሰጣል፣* የማቴ 21፥41 ማብ ይመ።

20፥17 *የማእዘን ራስ፣* የመዝ 118፥22 ማብ ይመ።

20፥18 *ይቀጠቀጣል፣* ከድንጋይ ጋር የሚላተም ሸክላ እንደሚሰበር፣ ድንጋይ ቍንከባሉ ያረፈበት ሸክላም እንደሚደቅ ሁሉ፣ መሢሑን ኢየሱስ አንቀበልም ያሉ ይፈረድባቸዋል (ኢሳ 8፥14 ይመ፤ ከዳን 2፥34-35፡ 44፤ ሉቃ 2፥34 ጋር ያነጻጽሩ)።

20፥19 *ጸሐፍትና፣* ኢየሱስን ስለ መቃወማቸው 5፥30፤ 9፥22፤ 19፥47፤ 22፥2፤ 23፥10 ይመ።

20፥20 *ለገዥው... ሥልጣን፣* የአይሁድ የሃይማኖት መሪዎች በራሳቸው ሥልጣን ርምጃ መውሰድ ስለ ፈሩ፣ ኢየሱስን በሚናገረው ቃል አጥምደው፣ ሮማውያን እርሱ ከሕዝቡ ጋር እንዳይገናኝ ርምጃ እንዲወስዱበት ሞከሩ።

ለማጥመድ ይከታተሉት ነበር፤ ስለዚህም ጻድቃን መስለው የሚቀርቡ ሰላዮችን ላኩበት። [21]ሰላዮቹም እንዲህ ሲሉ ጠየቁት፤ “መምህር ሆይ፤ አንተ ትክክለኛውን ነገር እንደምትናገርና እንደምታስተምር እንዲሁም የእግዚአብሔርን መንገድ በእውነት እንደምታስተምርና ለማንም እንደማታደላ እናውቃለን። [22]ለመሆኑ ለቄሳር ግብር መክፈል ይገባል ወይስ አይገባም?”

[23]እርሱ ግን ተንኰላቸውን ዐውቆ እንዲህ አላቸው፤ [24]“እስቲ አንድ ዲናር አሳዩኝ፤ በላዩ ያለው የማን መልክና ጽሕፈት ነው?”

[25]እነርሱም፣ “የቄሳር ነው” ብለው መለሱለት።

እርሱም፣ “እንግዲያውስ የቄሳርን ለቄሳር፣ የእግዚአብሔርንም ለእግዚአብሔር ስጡ” አላቸው።

[26]ስለዚህ በተናገረው ቃል በሕዝቡ ፊት ሊያጠምዱት አልቻሉም፤ በመልሱም ተገርመው ዝም አሉ።

### ትንሣኤ ሙታንና ጋብቻ

20፥27-40 ተጓ ምብ – ማቴ 22፥23-33፤ ማር 12፥18-27

[27]ትንሣኤ ሙታን የለም ከሚሉት ሰዱቃውያን አንዳንዶቹ ወደ ኢየሱስ መጥተው ጥያቄ አቀረቡለት፤ [28]እንዲህም አሉት፤ “መምህር ሆይ፤ አንድ ሰው ሚስት አግብቶ ልጅ ሳይወልድ ቢሞት፣ ወንድሙ መበለቲቱን አግብቶ ልጆች በመውለድ ለወንድሙ ዘር እንዲተካ ሙሴ ጽፎልናል። [29]ታዲያ፣ ሰባት ወንድማማቾች ነበሩ፤ የመጀመሪያው ሚስት አግብቶ ልጅ ሳይወልድ ሞተ፤ [30]ሁለተኛውም እንደዚሁ፤ [31]ሦስተኛው ደግሞ አገባት፤ ሰባቱም እንዲሁ እያሉ አግብተዋት ልጆች ሳይወልዱ ሞቱ። [32]በመጨረሻም ሴትዮዋ ሞተች። [33]እንግዲህ ሰባቱም ስላገቧት፣ በትንሣኤ ጊዜ የማን ሚስት ትሆናለች?”

[34]ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ “የዚህ ዓለም ልጆች ያገባሉ፤ ይጋባሉም፤ [35]የሚመጣውን ዓለምና የሙታንን ትንሣኤ ማግኘት የሚገባቸው ግን አያገቡም፤ አይጋቡም፤ [36]እንደ መላእክትም ስለሆኑ ከዚያ በኋላ አይሞቱም፤ የትንሣኤ ልጆች ስለ ሆኑም የእግዚአብሔር ልጆች ናቸው። [37]ሙሴ ስለ ቍጥቋጦ በተጻፈው ታሪክ ውስጥ ጌታን ‘የአብርሃም አምላክ፣ የይስሐቅ አምላክ፣ የያዕቆብ አምላክ’ በማለቱ ሙታን እንደሚነሡ ያሳያል፤ [38]ሁሉም ለእርሱ ሕያዋን ስለ ሆኑ፣ እርሱ የሕያዋን አምላክ እንጂ የሙታን አይደለም።”

[39]አንዳንድ ጸሐፍትም፣ “መምህር ሆይ፤ መልካም ተናገርህ” አሉት። [40]ከዚህ በኋላ አንድ ሰው እንኳ ሊጠይቀው አልደፈረም።

### ክርስቶስ የማን ልጅ ነው?

20፥41-47 ተጓ ምብ – ማቴ 22፥41-23፥7፤ ማር 12፥35-40

[41]ከዚህ በኋላ ኢየሱስ እንዲህ አላቸው፤ “ሰዎች ክርስቶስን[h] እንዴት የዳዊት ልጅ ነው ይሉታል? [42]ምክንያቱም ራሱ ዳዊት በመዝሙራት መጽሐፉ እንዲህ ብሏል፤

“ ‘ጌታ ጌታዬን፣
“በቀኜ ተቀመጥ፤
[43]እኔ ጠላቶችህን፣
ለእግርህ መርገጫ እስከማደርግልህ ድረስ።’ ”

[44]እንግዲህ ዳዊት እርሱን፣ ‘ጌታ’ ብሎ ሲጠራው እንዴት ልጁ ይሆናል?”

[45]ሕዝቡ ሁሉ እየሰሙትም ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው፤ [46]“ዘርፋፋ ቀሚስ ለብሰው መዞር ከሚወዱ፣ በገበያ ቦታ ሰላምታ ከሚሹና በምኵራብ የከበሬታ መቀመጫ፣ በግብዣ ቦታም የክብር ስፍራ ከሚፈልጉ፣ ከጸሐፍት ተጠንቀቁ፤ [47]እነርሱም የመበለቶችን ቤት የሚያራቁቱ ናቸው፤ ለታይታ ብለውም ጸሎታቸውን ያስረዝማሉ፤

20፥21 ዮሐ3፥2
20፥25 ሉቃ23፥2፤ ሮሜ13፥7
20፥27 ሐሥ 4፥1፤ 23፥8፤1ቆሮ15፥12
20፥28 ዘዳ25፥5
20፥35 ማቴ12፥32
20፥36 ዮሐ1፥12
20፥37 ዘፀ3፥6
20፥40 ማቴ12፥34፤ 22፥46
20፥41 ማቴ1፥1
20፥43 መዝ110፥1፤ ማቴ22፥44
20፥46 ሉቃ11፥43

h41 ወይም መሲሕ

20፥22 *ለቄሳር ግብር፤* ቄሳር የጣለውን ግብር መክፈል ትክክል ነው ብሎ መቀበሉ ሕዝቡን የሚያሳዝን ቢሆንም፣ ግብር እንዳይከፍሉ ማድረግ ደግሞ የሮም ባለሥልጣናትን የሚያስቈጣ ነበር፣ ስለዚህም ጠያቂዎቹ ኢየሱስን በዚህ ዐይነት አስቸጋሪ ጥያቄ ሊያጠምዱት አሰቡ።

20፥24 *አንድ ዲናር፤* የሮማ የገንዘብ ሳንቲም ሲሆን፣ ለአንድ ቀን ሥራ የሚከፈል ደመወዝ ነው (የማቴ 22፥19 ማብ ይመ)።

20፥25 *የእግዚአብሔርንም ለእግዚአብሔር፤* የማቴ 22፥21 ማብ ይመ።

20፥27 *ሰዱቃውያን፤* የገዥዎች ወገን የሆኑ፣ የፖለቲካ ስሜት የነበራቸውና ምድራዊ አመለካከት ከነበራቸው አረማውያን ጋር ኅብረት የሚያደርጉ ናቸው። በዚያን ጊዜ ከፍተኛውን የሊቀ ክህነት ሥልጣንን በእጃቸው ያስገቡና በአይሁድ ሸንጎ ውስጥም አብዛኛውን መቀመጫ የያዙ ነበሩ። በሙታን ትንሣኤ ወይም ከሞት በኋላ ሕይወት አለ ብለው አያምኑም፤ ፈሪሳውያን የሚያስተምሩትን፣ በቃል ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን የአበውን ልማድ አይቀበሉም፤ የሲፍ ወልደ ኩሪዮን፤ እንቲኩቲ 13፥10፥6 ይመ፤ የማቴ 2፥4፤ 3፥7፤ የማር 12፥18፤ ሐሥ 4፥1 ማብ ይመ።

20፥28 *ወንድሙ መበለቲቱን አግብቶ፤* አንድ ሰው ሳይወልድ ቢሞት፣ በሕይወት ያለ ወንድሙ ዘር እንዲተካለት በሚያዝዘው የሙሴ ሕግ መሠረት ማለት ነው (የማቴ 22፥24 ማብ ይመ፤ ከዘፍ 38፥8 ጋር ያነጻጽሩ)።

20፥34-35 *የዚህ ዓለምና... የሚመጣውን ዓለምና፤* የ18፥30 ማብ ይመ።

20፥36 *እንደ መላእክትም፤* የትንሣኤ ሁኔታ፣ የአሁኑን ዓለም ሥርዐት ይከተላል ብሎ ማሰብ አይቻልም። በአዲሱ ዘመን ጋብቻና ሞት የለም። *የትንሣኤ ልጆች፤* በጻድቃን ትንሣኤ ወቅት የሚነሡ ምእመናን ናቸው (ከማቴ 22፥23-33፤ ማር 12፥18-27፤ ሐሥ 4፥1-2፤ 23፥6-10 ጋር ያነጻጽሩ)።

20፥37 *ስለ ቍጥቋጦ በተጻፈው ታሪክ፤* ክርስቶስ በዚህ ምድር በነበረበት ወቅት፣ ቅዱሳት መጻሕፍት በምዕራፍና በቍጥር ስላልተከፋፈሉ፣ ሙሴ የሚቃጠለውን ቍጥቋጦ ያየበት ምንባብ የሚጠቀሰው በዚህ መልክ ነበር (ዘፀ 3፥2)።

20፥39 *መምህር ሆይ፣ መልካም ተናገርህ፤* ከፈሪሳውያን ወገን የሆኑት እነዚህ ጸሐፍት በኢየሱስ ላይ ከፍተኛ ጥላቻ ቢኖራቸውም፣ የትንሣኤ ጒዳይ ሲነሣ ግን፣ ሰዱቃውያንን ተቃውመው የኢየሱስን ሐሳብ ደገፉ።

20፥44 *ዳዊት... ‘ጌታ’ ብሎ ሲጠራው፤* መሲሑ ከዳዊት ዘር ከሆነ፣ ታዲያ ይህ የተከበረ ንጉሥ ልጁን እንዴት ‘ጌታ’ ብሎ ሊጠራው ይችላል? እነዚህ የኢየሱስ ተቃዋሚዎች፣ መሲሑ የእግዚአብሔር የባሕርይ ልጅ መሆኑን ለመቀበል የተዘጋጁ ካልሆኑ በቀር፣ ለዚህ ጥያቄ መልስ መስጠት አይችሉም። የመዝ 110፥1 ማብ ይመ።

20፥46 *ዘርፋፋ ቀሚስ... የከበሬታ መቀመጫ፤* የማር 12፥38-39 ማብ ይመ።

20፥47 *የመበለቶችን ቤት የሚያራቁቱ፤* ለግል ጥቅማቸው ሲሉ፣ እነዚህን ረዳት የሌላቸውን ሴቶች በማታለል ወጥ

እነዚህ የከፋ ፍርድ ይጠብቃቸዋል።"

## መበለቷ የሰጠችው መባ

21፥1-4 ተጓ ምብ-ማር 12፥41-44

**21** ኢየሱስ ቀና ብሎ ሲመለከት ሀብታሞች በቤተ መቅደሱ መባ መሰብሰቢያ ውስጥ መባቸውን ሲጨምሩ አየ። 2ደግሞም አንዲት ድኻ መበለት ሁለት ትናንሽ የናስ ሳንቲሞች በዚያ ስትጨምር ተመለከተ፤ 3እንዲህም አለ፤ "እውነት እላችኋለሁ፤ ከሁሉም ይልቅ ይህች ድኻ መበለት የበለጠ ሰጥታለች፤ 4እነዚህ ሰዎች የሰጡት ከትርፋቸው ላይ ሲሆን፣ እርሷ ግን የሰጠችው በድኻ ዐቅሟ ያላትን መተዳደሪያ በሙሉ ነው።"

## የዘመኑ መጨረሻ ምልክቶች

21፥5-36 ተጓ ምብ – ማቴ 24፤ማር13
21፥12-17 ተጓ ምብ – ማቴ 10፥17-22

5ከደቀ መዛሙርት አንዳንዶች ቤተ መቅደሱ በውብ ድንጋዮችና በስእለት ስጦታዎች እንዳማረ ሲነጋገሩ፣ ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ 6"ይህ የምታዩት ሁሉ ሳይፈርስ ድንጋይ በድንጋይ ላይ እንደ ተካበ የማይቀርበት ጊዜ ይመጣል።"

7እነርሱም፣ "መምህር ሆይ፤ እንግዲህ ይህ ሁሉ የሚሆነው መቼ ነው? ደግሞም ይህ እንደሚሆን ምልክቱ ምንድን ነው?" ብለው ጠየቁት።

8እርሱም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "እንዳትስቱ ተጠንቀቁ፤ ብዙዎች፣ 'እኔ እርሱ ነኝ' በማለት፣ ደግሞም፣ 'ጊዜው ቀርቦአል' እያሉ በስሜ ይመጣሉና፤ እናንተ ግን እነርሱን አትከተሏቸው። 9ስለ ጦርነትና ስለ ሕዝብ ዐመፅ ስትሰሙ አትደንግጡ፤ ይህ አስቀድሞ መሆን የሚገባው ነውና፤ መጨረሻው ግን ወዲያውኑ አይሆንም።"

10ቀጥሎም እንዲህ አላቸው፤ "ሕዝብ በሕዝብ ላይ፣ መንግሥትም በመንግሥት ላይ ይነሣል፤ 11ታላቅ የመሬት መናወጥ ይሆናል፤ ራብና ቸነፈር በተለያየ ስፍራ ይከሠታል፤ አስፈሪ ነገር እንዲሁም ከሰማይ ታላቅ ምልክት ይሆናል።

12"ይህ ሁሉ ከመሆኑ በፊት ግን ሰዎች ይይዟችኋል፤ ያሳድዷችኋል፤ ወደ ምኵራብና ወደ ወህኒ ቤት ያስገቧችኋል፤ በነገሥታትና በገዦች ፊት ያቀርቧችኋል፤ ይህም ሁሉ በስሜ ምክንያት ይደርስባችኋል። 13ይህም ለመመስከር ጥሩ ዕድል ይሆንላችኋል። 14ስለዚህ ምን መልስ እንሰጣለን በማለት አስቀድማችሁ እንዳትጨነቁ ይህን ልብ በሉ፤ 15ተቃዋሚዎቻችሁ ሁሉ ሊቋቋሙትና ሊያስተባብሉት የማይችሉትን ቃልና ጥበብ እሰጣችኋለሁና። 16ወላጆቻችሁ፣ ወንድሞቻችሁ፣ ዘመዶቻችሁና ጓደኞቻችሁ እንኳ ሳይቀሩ አሳልፈው ይሰጡአችኋል፤ ከእናንተም አንዳንዶቹን ይገድላሉ፤ 17ስለ ስሜም በሰዎች ሁሉ ዘንድ የተጠላችሁ ትሆናላችሁ። 18ነገር ግን ከራሳችሁ ጠጕር አንዲ እንኳ አትጠፋም፤ 19ጸንታችሁም በመቆም ነፍሳችሁን ታተርፋላችሁ።

20"ኢየሩሳሌም በጦር ሰራዊት ተከባ በምታዩበት ጊዜ፣ ጥፋቷ መቃረቡን ዕወቁ። 21በዚያን ጊዜ በይሁዳ ያሉ ወደ ተራሮች ይሽሹ፤ በከተማ ያሉትም ከዚያ ይውጡ፤ በገጠር ያሉትም ወደ ከተማዪቱ አይግቡ፤ 22የተጻፈው ሁሉ ይፈጸም ዘንድ ይህ የበቀል ጊዜ ነውና። 23በምድሪቱ ላይ ታላቅ

21፥1 ማቴ27፥6፤ ዮሐ8፥20
21፥4 2ቆሮ8፥12
21፥6 ሉቃ19፥44
21፥8 ሉቃ17፥23
21፥10 2ዜና15፥6፤ ኢሳ19፥2
21፥11 ኢሳ29፥6፤ ኢል2፥30
21፥13 ፊል1፥12
21፥14 ሉቃ12፥11
21፥15 ሉቃ12፥12
21፥16 ሉቃ12፥52፡53
21፥17 ዮሐ15፥21
21፥18 ማቴ10፥30
21፥19 ማቴ10፥22
21፥20 ሉቃ19፥43
21፥21 ሉቃ17፥31
21፥22 ኢሳ63፥4፤ ዳን9፥24-27፤ ሆሴ 9፥7፤ማቴ1፥22

---

መዳቸው ውስጥ ያስገቡአቸዋል። *የከፋ ፍርድ ይጠብቃቸዋል፤* ከ12፥47-48 ጋር ያነጻጽሩ። በሰው ዘንድ መልካም ግምት ማግኘት በጨመረ ቍጥር፣ ያንኑ ያህል መልካም አርአያነት ይጠበቃል፤ ግብዝነትም በጨመረ ቍጥር (ማቴ 23፥1-36)፣ በዚያው መጠን የባሰ ፍርድ ይደርስባቸዋል።

21፥1 *በቤተ መቅደሱ መባ መሰብሰቢያ፤* በቤተ መቅደሱ የሴቶች መቆሚያ በኩል፣ የቀለምሸሸ እግር ቅርጽ ያላቸው 13 ሣጥኖች ነበሩ፤ እነዚህም ለአምልኮ ከሚመጡ ምእመናን ምጽዋት ለመሰብሰብ በሚያመች ሁኔታ ተቀምጠው ነበር።

21፥2 *ትናንሽ የናስ ሳንቲሞች፤* የአይሁዳውያን ሳንቲሞች ዋጋቸው አነስተኛ ነው።

*21፥3-4፤* የ2 ቆሮ 8፥12 ማብ ይመ።

*21፥5-36፤* የማር 13፥1-37 ማብ ይመ።

21፥5 *ቤተ መቅደሱ ... እንዳማረ፤* በደቡብ ምዕራብ በኩል ከነበሩት ድንጋዮች መካከል አንዱ 11 ሜትር ያህል ይረዝም ነበር። "በወርቅ ያልተለበጠ ድንጋይ ሁሉ፣ እጅግ የነጣ እንደ ነበር'' ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን ጽፎአል (የአይሁዳ ጦርነት 5.5.6)። ሄሮድስም ለአንዱ ማጌጫ ይሆን ዘንድ ወርቅማ የወይን ተክል ሰጥቷል።

21፥6 *ይህ... ድንጋይ ... የማይቀርበት፤* በ70 ዓ.ም ሮማውያን ኢየሩሳሌምን በመያዝ ቤተ መቅደሱን ባቃጠሉ ጊዜ ይህ ትንቢት ተፈጽሞአል (የማቴ 24፥2 ማብ ይመ)።

21፥7 *መቼ ነው?* ማርቆስ ይህ ጥያቄ በአራቱ ደቀ መዛሙርት ማለትም በጴጥሮስ፣ በያዕቆብ፣ በዮሐንስና በእንድርያስ እንደ ቀረበ ጽፎአል (ማር 13፥3)፤ ማቴዎስ የጥያቄውን አቀራረብ በዝርዝር የጻፈው ሲሆን፣ ይኸውም የኢየሱስ መምጣትና የዘመኑ ፍጻሜ ምልክት ምን እንደሆነም ይገኝበታል (ማቴ 24፥3)። *ምልክቱ ምንድን ነው?* እነዚህ ነገሮች እንደሚፈጸሙ ማረጋገጫው ምንድን ነው? ማለት ነው።

21፥8 *'እኔ እርሱ ነኝ'፤* ዳግም የመጣሁት መሲሑ ኢየሱስ እኔ ነኝ ይላሉ ማለት ነው። *ጊዜው፤* የዘመኑ ፍጻሜ ማለት ነው።

21፥9 *መጨረሻው ግን ወዲያውኑ አይሆንም፤* የዘመኑን ፍጻሜ ያመለክታል (ማቴ 24፥3፡6 ይመ)። በቍ 8-18 ባለው ላይ የተዘረዘሩት የመጨረሻው ዘመን ምልክቶች ብቻ ሳይሆኑ፣ የአሁኑም ዘመን ባሕርያት ናቸው።

21፥11 *ከሰማይም ታላቅ ምልክት፤* ቍ 25 ይመ። በጌታ ቀን ከሰማይ ስለሚሆነው ምልክት የተነገረውን የትንቢት ቃል በተመለከተ ማር 13፥25 ማብ ይመ።

21፥12 *ወደ ምኵራብና... ያስገቧችኋል፤* ምኵራቦች አገልግሎት የሚሰጡት ለአምልኮና ለትምህርት ብቻ ሳይሆን፣ ለአስተዳደርና ፍርድ ቤት የሚቀርቡትንም ሰዎች ለጊዜው ለማቆያም ጭምር ነበር።

21፥15 *ሊቋቋሙት... የማይችሉት፡፡* ሐሥ 6፥9-10 ይመ።

*21፥18፤* ስደትና ሞት ቢደርስባቸውም፣ በእግዚአብሔር ቍጥጥር ሥር ነው፤ በመጨረሻም ዘላለማዊ ድል የእነርሱ ይሆናል። *ከራሳችሁ ጠጕር አንዷ እንኳ አትጠፋም፤* ከቍ 16 አኳያ ሲታይ፣ ምንም ዐይነት ጕዳት እንደማይደርስባቸው አያመለክትም፤ ተለዋጭ ዘይቤው የሚያመለክተው በመንፈሳዊ ሕይወት ረገድ ምንም ዐይነት ኪሳራ እንደማይደርስባቸው ነው።

*21፥19፤* የማር 13፥13 ማብ ይመ።

21፥20 *በጦር... ተከባ፤* 19፥43 ይመ። የዘመኑ ፍጻሜ ለመድረሱ ምልክቱ (ከቍ7 ጋር ያነጻጽሩ)፣ የኢየሩሳሌም በጦር መከበብ ነው፤ ከዚህ ጋር ተያይዞ የሚመጣው 'የጥፋት ርኩሰት' ነው (ማቴ 24፥15)።

21፥21 *ወደ ተራሮች ይሽሹ፤* የጠላት ጦር አንድን ከተማ ሲከብ፣ በምሽጎች ውስጥ መሸሸግ የተለመደ ነው፤ ኢየሱስ ግን ተከታዮቹ ተራሮችን መጠጊያ እንዲያደርጉ አዘዘ፤ ይህም ከተማዋ እንደምትጠፋ ያመለክታል (የማቴ 24፥16 ማብ ይመ)።

21፥22 *የበቀል ጊዜ፤* በማያምኑ ላይ፣ እግዚአብሔር የሚያመ

መከራ ይሆናል፤ በዚህም ሕዝብ ላይ ቍጣ ይመጣል፤ ስለዚህ በዚያን ወቅት ለነፍሰጡሮችና ለሚያጠቡ እናቶች ወዮላቸው! [24]በሰይፍ ይወድቃሉ፤ ወደ አሕዛብም ሁሉ በምርኮ ይወሰዳሉ፤ ኢየሩሳሌምም የአሕዛብ ዘመን እስኪፈጸም ድረስ፣ በአሕዛብ የተረገጠች ትሆናለች።

[25]"በፀሐይ፣ በጨረቃና በከዋክብት ላይ ምልክት ይሆናል፤ ከባሕሩና ከሞገድ ድምፅ የተነሣ፣ በምድር ላይ ያሉ ሕዝቦች ይጨነቃሉ፤ ይታወካሉም፤ [26]የሰማያት ኀይላት ስለሚናወጡ፣ ሰዎች በፍርሀትና በዓለም ላይ ምን ይመጣ ይሆን እያሉ በመጠባበቅ ይዝላሉ። [27]በዚያን ጊዜ የሰው ልጅ በኀይልና በታላቅ ክብር በደመና ሲመጣ ያዩታል። [28]እናንተም እነዚህ ነገሮች መፈጸም ሲጀምሩ፣ መዳናችሁ ስለ ተቃረበ፣ ቀጥ ብላችሁ ቁሙ፤ ራሳችሁንም ወደ ላይ ቀና አድርጉ።"

[29]ቀጥሎም እንዲህ ሲል ይህን ምሳሌ ነገራቸው፤ "በለስንና ዛፎችን ሁሉ ተመልከቱ፤ [30]ቅጠሎቻቸው አቈጥቍጠው ስታዩ፣ በዚያን ጊዜ በጋ መቃረቡን ራሳችሁ ታውቃላችሁ። [31]እንዲሁ ደግሞ እነዚህ ነገሮች መፈጸማቸውን ስታዩ፣ የእግዚአብሔር መንግሥት እንደ ቀረበች ዕወቁ።

[32]"እውነት እላችኋለሁ፤ ይህ ሁሉ እስኪፈጸም ድረስ ይህ[h] ትውልድ አያልፍም። [33]ሰማይና ምድር ያልፋሉ፤ ቃሌ ግን አያልፍም።"

[34]"እንግዲህ በገደብ የለሽ ሕይወት፣ በመጠጥ ብዛትና ስለ ኑሮ በመጨነቅ ልባችሁ እንዳይዝልና ያ ቀን እንደ ወጥመድ ድንገት እንዳይደርስባችሁ ተጠንቀቁ፤ [35]ይህ በመላው ምድር በሚኖሩት ሁሉ ላይ ይደርሳልና። [36]ስለዚህ ከሚመጣው ሁሉ እንድታመልጡና በሰው ልጅ ፊት መቆም እንድትችሉ ሁልጊዜ ተግታችሁ ጸልዩ።"

[37]ኢየሱስም ቀን ቀን በቤተ መቅደስ እያስተማረ፣ ሌሊት ግን ደብረ ዘይት ወደ ተባለ ተራራ ወጥቶ ያድር ነበር። [38]ሕዝቡም ሁሉ ሊሰሙት ማልደው ወደ ቤተ መቅደስ ወደ እርሱ ይመጡ ነበር።

## ይሁዳ ጌታን አሳልፎ ለመስጠት ተስማማ

22፥1:2 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥2-5፤ ማር 14፥1:2፡ 10:11

**22** በዚህ ጊዜ ፋሲካ የተባለው የቂጣ በዓል ተቃርቦ ነበር። [2]የካህናት አለቆችና ጸሐፍትም ሕዝቡን ይፈሩ ስለ ነበር፣ እንዴት አድርገው ኢየሱስን እንደሚያስወግዱት መንገድ ይፈልጉ ነበር። [3]ሰይጣንም ከዐሥራ ሁለቱ ጋር በተቈጠረው የአስቆሮቱ ይሁዳ በተባለው ገባበት፤ [4]ይሁዳም ወደ ካህናት አለቆችና ወደ ቤተ መቅደሱ ሹሞች ሄዶ ኢየሱስን እንዴት አሳልፎ እንደሚሰጣቸው ተነጋገረ። [5]እነርሱም በዚህ ደስ ተሰኝተው፣ ገንዘብ ሊሰጡት ተዋዋሉ። [6]እርሱም በነገሩ ተስማማ፤ አሳልፎ ሊሰጣቸውም ሕዝብ የማይገኝበትን ምቹ ጊዜ ይጠብቅ ጀመር።

21፥24 ኢሳ5፥5፤ 63፥18፤ ዳን8፥13፤ ራእ11፥2
21፥25 2ጴጥ3፥10:12
21፥26 ማቴ24፥29
21፥27 ማቴ8፥20፤ ራእ1፥7
21፥28 ሉቃ18፥7
21፥31 ማቴ3፥2
21፥32 ሉቃ 11፥50፤17፥25
21፥33 ማቴ5፥18
21፥34 ማር4፥19፤ ሉቃ12፥40:46፤ 1ተሰ5፥2-7
21፥36 ማቴ26፥41
21፥37 ማቴ21፥1፤ 26፥55፤ ማር11፥19
21፥38 ዮሐ8፥2
22፥1 ዮሐ11፥55
22፥2 ማቴ12፥14
22፥3 ማቴ4፥10፤ ማቴ10፥4
22፥4 ቍ52፤ ሐሥ4፥1፤5፥24
22፥5 ዘካ11፥12

[h]32 *ወይም ዘር*

ጣው ፍትሐዊ ቅጣት ነው (ከኢሳ 63፥4፤ ኤር 5፥29፤ ሆሴ 9፥7 ጋር ያነጻጽሩ)።

21፥24 *የአሕዛብ ዘመን፤* አሕዛብ፣ መንፈሳዊና (ማር13፥10፤ ከሉቃ 20፥16፤ ሮሜ 11፥25 ጋር ያነጻጽሩ) በኢየሩሳሌም ላይ የበላይ የመሆን ዕድል ይኖራቸዋል፤ ይሁን እንጂ እግዚአብሔር ለእነርሱ ያለው ዕቅድ ሲፈጸም ይህ ጊዜ ያበቃል።

21፥27 *በዚያን ጊዜ የሰው ልጅ...ሲመጣ፤* የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ማለት ነው (ዳን 7፥13 ይመ)፤ በዚህ ንግግር ውስጥ ያለው ሐሳብ የመጨረሻውን ዘመን የሚያመለክት ቢሆንም፣ በ70 ዓ.ም የተፈጸመውን የኢየሩሳሌምን መፈራረስ ይመለከታል።

21፥28 *ራሳችሁንም... ቀና አድርጉ፤* እነዚህ ምልክቶች በሚታዩበት ጊዜ አትደንግጡ፤ ነገር ግን በደስታ፣ በተስፋና በእምነት ተመልከቱት። *መዳናችሁ፤* ፍጹምና ሙሉ በሙሉ መዳናችሁ ማለት ነው።

21፥29 *በለስንና ዛፎችን... ተመልከቱ፤* የፀደይ ወራት መግባቱ የሚታወቀው፣ ዛፎች ለምልመው ሲታዩ ነው (ከማቴ 24፥32-35፤ ማር 13፥28-31 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ልክ እንደዚሁ የእግዚአብሔርም መንግሥት መምጣት የሚታወቀው፣ የመምጣቱ ምልክቶች ሲታዩ ነው። ይሁን እንጂ "መንግሥት" የሚለው ቃል በልዩ ልዩ መንገድ ጥቅም ላይ ውሎአል (የ4፥43 ማብ ይመ)። በቍ 31 ላይ የሚገኘው፣ ወደፊት የሚመጣውን መንግሥት የሚያሳየው ነው።

21፥32 *ይህ ትውልድ፤* ኢየሱስ ይህን ከተናገረ ከ40 ዓመት በኋላ የተፈጸመውን የኢየሩሳሌምን መፈራረስ የሚመለከት ከሆነ፣ ትውልድ የሚለው ቃል የአንድን ሰው የሕይወት ዘመን የሚመለከት ነው፤ ትንቢቱም ኢየሩሳሌም በ70 ዓ.ም. ስትፈራርስ ተፈጽሞአል። በሌላ በኩል ግን፣ ይህ የሚያሳየው የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ከሆነ፣ "ትውልድ" የሚለው ቃል እስከ መጨረሻው ዘመን እንደሚኖሩ ተስፋ የተሰጣቸውን የአይሁድን ሕዝብ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል፤ (አማራጭ ትርጕሙን ይመ)፤ ወይም እነዚህ ትንቢቶች መፈጸም በሚጀምሩበት ጊዜ የሚኖሩትን የወደፊቱን ትውልድ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል።

21፥34 *ያ ቀን፤* ክርስቶስ ዳግም የሚመጣበትና የእግዚአብሔር መንግሥት በሙሉ ክብር የሚገለጥበት ነው (ከቍ 31 ጋር ያነጻጽሩ)። *ድንገት እንዳይደርስባችሁ፤* ክርስቶስ ዳግም በሚመጣበት ጊዜ የሚታዩ ምልክቶች ስላሉ፣ የክርስቶስ ዳግም ምጽአት ፈጽሞ አይታወቅም ማለት አይቻልም (ቍ 28:31)።

21፥35 *በመላው ምድር፤* በኢየሩሳሌም መፍረስ የደረሰው ጉዳት በራሷ በከተማዋ ላይ ብቻ ሲሆን፣ በክርስቶስ ዳግም ምጻት የሚሆነው ግን ሁሉንም ይመለከታል።

21፥37 ቀን ቀን፤ በመጨረሻው ሳምንት፣ ማለትም በክብር ወደ ኢየሩሳሌም ከገባበት ጊዜ ጀምሮ እስከ ፋሲካ ድረስ (ከእሁድ እስከ ሐሙስ) ማለት ነው። *ደብረ ዘይት ... ተራራ፤* የ19፥29፤ ማቴ 21፥17 ማብ ይመ።

22፥1 *ፋሲካ ... የቂጣ በዓል፤* "ፋሲካ"፣ በሁለት መንገድ ይታወቅ ነበር 1)የኒሳን ወር በገባ በዐሥራ አራተኛው ቀን ምሽት የሚበላው ልዩ ምግብ ሲሆን (ዘሌ 23፥4-5)፣ 2) የፋሲካ ምግብ ከተበላ በኋላ ያለው ሳምንት ነው (ሕዝ 45፥21)፣ ይህም የቂጣ በዓል በመባልም የሚታወቅ ሲሆን፣ እርሾ ያልገባበት ምግብም የሚበላበት ሳምንት ነው (ዘፀ 12፥15-20፤ 13፥3-7)። በአዲስ ኪዳን ዘመን ይህ ሳምንት ሙሉ የሚከበረው በዓል፣ በሁለቱም ስሞች (ፋሲካ ወይም የቂጣ በዓል በመባል) ይጠራ ነበር።

22፥2 *የካህናት አለቆችና ጸሐፍትም፤* 20፥1 ይመ።

22፥3 *ሰይጣን...ይሁዳ በተባለው ገባበት፤* ይህ አገላለጽ በወንጌላት ውስጥ በሁለት የተለያዩ ጊዜያት ተጠቅሶአል 1) ይሁዳ ኢየሱስን አሳልፎ ለመስጠት ወደ ካህናት አለቆች ከመሄዱ በፊትና 2) በመጨረሻው ራት ጊዜ ነው (ዮሐ 13፥27)። ኢየሱስን የማገልገልና ሕይወቱንም ለእርሱ የማስረከብ ዝንባሌ ከቶ ያልነበረውን ይሁዳን፣ ሰይጣን ምን ያህል በቍጥጥሩ ሥር እንዳደረገው፣ ወንጌል ጸሐፊዎቹ በግልጽ አሳይተዋል።

22፥4 *ወደ ቤተ መቅደሱ ሹሞች፤* እነዚህ ሁሉም አይሁዳውያን ነበሩ፤ አብዛኛዎቹም የተመረጡት ከሌዊ ወገን ነው።

## የመጨረሻው እራት

22፥7-13 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥17-19፤ ማር 14፥12-16
22፥17-20 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥26-29 ማር 14፥22-25፤1 ቆሮ 11፥23-25
22፥21-23 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥21-24፤ ማር 14፥18-21፤ ዮሐ 13፥21-30
22፥25-27 ተጓ ምብ – ማቴ 20፥25-28፤ ማር 10፥42-45
22፥33-34 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥33-35፤ ማር 14፥29-31፤ ዮሐ 13፥37-38

7ከዚህ በኋላ የፋሲካ በግ የሚታረድበት የቂጣ በዓል ደረሰ። 8ኢየሱስም፣ “የፋሲካን እራት እንድንበላ ሄዳችሁ አዘጋጁልን” ብሎ ጴጥሮስንና ዮሐንስን ላካቸው።

9እነርሱም፣ “የት እንድናሰናዳ ትፈልጋለህ?” አሉት።

10እርሱም እንዲህ አላቸው፤ “እነሆ፤ ወደ ከተማ ስትገቡ የውሃ እንስራ የተሸከመ ሰው ያገኛችኋል፤ እርሱ ወደሚገባበት ቤት ድረስ ተከተሉት፤ 11ለቤቱም ባለቤት፣ ‘መምህሩ፣ “ከደቀ መዛሙርቴ ጋር የፋሲካን እራት የምበላበት የእንግዳ ክፍል ወዴት ነው?” ይልሃል’ በሉት። 12እርሱም በሰገነት ላይ ያለውን ተነጥፎ የተዘጋጀ ሰፊ አዳራሽ ያሳያችኋል፤ በዚያም አሰናዱልን።”

13እነርሱም ሄደው ልክ ኢየሱስ እንደ ነገራቸው ሆኖ አገኙት፤ ፋሲካንም በዚያ አዘጋጁ።

14ሰዓቱም በደረሰ ጊዜ ኢየሱስ ከሐዋርያቱ ጋር በማእድ ተቀመጠ፤ 15እንዲህም አላቸው፤ “መከራ ከመቀበሌ በፊት ይህን ፋሲካ አብሬያችሁ ለመብላት በጣም ስመኝ ነበር፤ 16እላችኋለሁ፤ በእግዚአብሔር መንግሥት የዚህ ትርጒም እስኪፈጸም ድረስ ይህን ፋሲካ ዳግመኛ አልበላም።”

17ጽዋውን ተቀብሎ ካመሰገነ በኋላ እንዲህ አላቸው፤ “እንካችሁ፤ ሁላችሁ ከዚህ ተካፈሉ፤ 18እላችኋለሁና፤ ከአሁን ጀምሮ የእግዚአብሔር መንግሥት እስከምትመጣ ድረስ፣ ከዚህ ወይን ፍሬ አልጠጣም።”

19እንጀራንም አንሥቶ አመሰገነ፤ ቈርሶም ሰጣቸውና፣ “ይህ ስለ እናንተ የሚሰጥ ሥጋዬ ነው፤ ይህን ለመታሰቢያዬ አድርጉት” አለ።

20እንደዚሁም ከእራት በኋላ ጽዋውን አንሥቶ እንዲህ አለ፤ “ይህ ጽዋ ስለ እናንተ በሚፈሰው ደሜ የሚመሠረት አዲስ ኪዳን ነው። 21ነገር ግን አሳልፎ የሚሰጠኝ ሰው እጅ በማእድ ከእኔ ጋር ናት። 22የሰው ልጅስ አስቀድሞ በተወሰነው መሠረት ይሄዳል፤ ነገር ግን እርሱን አሳልፎ ለሚሰጠው ለዚያ ሰው ወዮለት።” 23እነርሱም ከመካከላቸው ይህን የሚያደርግ ማን ሊሆን እንደሚችል እርስ በርሳቸው ይጠያየቁ ጀመር።

24ደግሞም ከመካከላቸው ማን እንደሚበልጥ በእነርሱ ዘንድ ክርክር ተነሣ። 25ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፤ “የአሕዛብ ነገሥታት ሕዝቦቻቸውን በኀይል ይገዛሉ፤ በእነርሱ ላይ ሥልጣን ያላቸውም በጎ አድራጊዎች ተብለው ይጠራሉ። 26በእናንተ ዘንድ ግን እንዲህ አይሁን፤ ይልቁን ከእናንተ ታላቅ የሆነ እንደ ታናሽ፣ ገዥ የሆነም እንደ አገልጋይ ይሁን። 27ለመሆኑ፣ በማእድ ከተቀመጠና ቆሞ ከሚያስተናግድ ማን ይበልጣል? በማእድ የተቀመጠው አይደለምን? እኔ ግን በመካከላችሁ ያለሁት እንደ አንድ አገልጋይ ነው። 28እናንተም ሳትለዩኝ በመከራዬ ጊዜ በአጠገቤ የቆማችሁ ናችሁ፤ 29አባቴ እኔን እንደ ሾመኝ እኔም ደግሞ በመንግሥቴ እሾማችኋለሁ፤

22፥7 ዘፀ12፥18-20፤ ዘዳ16፥5-8፤ ማር14፥12
22፥8 ሐሥ3፥1፡ 11፤ 4፥13፡19፤8፥14
22፥13 ሉቃ19፥52
22፥14 ማቴ26፥20፤ማር6፥30 14፥17፡18
22፥15 ማቴ16፥21
22፥16 ሉቃ14፥15
22፥19 ማቴ14፥19
22፥20 ዘፀ24፥8፤ ኢሳ 42፥6፤ ኤር31፥31-34 ዘካ9፥11፤ 2ቆሮ3፥6፤ ዕብ8፥6፣9፥15
22፥21 መዝ41፥9
22፥22 ማቴ8፥20፤ ሐሥ2፥23፤4፥28
22፥24 ማር9፥34፤ ሉቃ9፥46
22፥26 ማር9፥35፤ 1ጴጥ5፥5
22፥27 ማቴ20፥28
22፥29 ማቴ25፥34፤ 2ጢሞ2፥12
22፥30 ማቴ19፥

22፥7 *የፋሲካ በግ የሚታረድበት*፤ የኒሳን ወር በገባ በ14ኛው ቀን፣ በሰሞን ሐምሌት ሐሙስ ቀን ከሰዓት በኋላ ከ8:30-11:30 ባለው ሰዓት፣ ካህናቱ በሚቆሙበት ስፍራ ማለት ነው።

22፥10 *የውሃ እንስራ የተሸከመ ሰው*፤ ውሃ በእንስራ መሸከም የሴት እንጂ የወንድ ሥራ ባለመሆኑ፣ አንድ ሰው ውሃ በእንስራ ተሸክሞ መታየቱ ጨርሶ ያልተለመደ ነው።

22፥11 *መምህሩ... ይልሃል*፤ ይህ ጥያቄ በዚህ ዐይነት መገለጹ፣ ኢየሱስ የእርሱ ተከታይ መሆኑን ስለሚያውቅ ሊሆን ይችላል።

22፥13 *ኢየሱስ እንደ ነገራቸው*፤ የፋሲካ እራት መብላታቸው እንዳይስተጓጐል፣ ኢየሱስ አስቀድሞ ከሰውየው ጋር በመነጋገር ሁኔታዎችን አመቻችቶ ሊሆን ይችላል። ኢየሱስ የፋሲካን እራት የት እንደሚበሉ ለደቀ መዛሙርቱ አስቀድሞ ስላልነገራቸው፣ ኢየሱስ የት እንደሚገኝ ይሁዳ ለጠላቶቹ በመንገር ይህን ልዩ ጊዜ እንዳይስተጓጐል አድርጎታል።

*22፥14-30*፤ ሉቃስ የመጨረሻውን እራት ሁኔታ ሲተርክ፣ የነገሮችን ቅደም ተከተል ጠብቆ ለመግለጽ ጥረት ያደረገ አይመስልም፤ ነገር ግን በወቅቱ ከተከናወኑት መካከል ዐቢይ የሆነውን ነገር ብቻ ይኸውም፣ እንጀራውንና ጽዋውን በጋራ መካፈላቸውን በመጀመሪያ ጽፎታል። ምንም እንኳ እነዚህ ሁለት ጒዳዮች ቀደም ብለው የቀረቡ ቢሆኑም፣ ሉቃስ ቀጥሎ የጻፈው ኢየሱስ አሳልፎ ስለሚሰጠው የተናገረውንና ከደቀ መዛሙርት መካከል ማን ታላቅ ይሆናል በሚለው ጒዳይ ላይ ነው።

22፥14 *በማእድ ተቀመጠ*፤ የማር 14፥3 ማብ ይመ።

22፥16 *እስኪፈጸም ድረስ*፤ ኢየሱስ ራሱ “የፋሲካ በግ” ሆኖ (1ቆሮ 5፥7) ከመታረዱ በፊት፣ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር የፋሲካን እራት ለመብላት ያለው የመጨረሻ ጊዜ ይህ ብቻ በመሆኑ፣ ይህን ጊዜ ይናፍቀው ነበር። የእግዚአብሔር መንግሥት እስከሚመጣ ድረስ ኢየሱስ ይህን ዐይነት የፋሲካ እራት ከእንግዲህ ወዲያ አይበላም። ከዚህ በኋላ ግን በዘመናት ሁሉ የጌታ እራት ከሚካፈሉት ሁሉ ጋር ኅብረት በየጊዜው ያደርጋል፤ ይህ ኅብረትም፣ ወደ ፊት በሚከናወነው በመሲሑ ታላቅ ‘የሰርግ እራት’ ላይ ይከበራል (ራእ 19፥9)።

22፥17 *ጽዋውን ተቀብሎ*፤ የፋሲካ እራት በሚበላ በት ወቅት ከሚቀርቡት አራት ጽዋዎች መካከል የመጀመሪያው ወይም ሦስተኛው ጽዋ ሊሆን ይችላል።

22፥18 *የእግዚአብሔር መንግሥት እስከምትመጣ ድረስ*፤ የቍ 16፤4፥43 ማብ ይመ።

22፥19 *ስለ እናንተ የሚሰጥ*፤ በመስቀል ላይ ቤዛ ሆኖ እንደ ሚሠዋ የሚያመለክት ነው። *ለመታሰቢያዬ*፤ እግዚአብሔር፣ እስራኤላውያንን ከግብፅ ባርነት ነጻ እንዳወጣቸው የፋሲካ በዓል ዘወትር እንደሚያስታውሳቸው ሁሉ፣ ይህን የክርስቶስ ትእዛዝ መጠበቅም፣ በክርስቶስ ቤዛዊ የመስቀል ሞት አማኞች ከኀጢአት እስራትና ባርነት ነጻ መውጣታቸውን ያስታውሳል።

22፥20 *ከእራት በኋላ*፤ ይህ የሚገኘው በዚህ ምንባብና በ1ቆሮ 11፥25 ላይ ብቻ ነው፤ የ1ቆሮ 11፥23-26 ማብ ይመ። *ጽዋውን አንሥቶ*፤ የማር 14፥24 ማብ ይመ። *አዲስ ኪዳን* እግዚአብሔር ቸርነቱን በሙላት እንደሚሰጥ በነቢዩ ኤርሚያስ በኩል ተስፋ የሰጠ ሲሆን (31፥31-34) ይህም በኢየሱስ ሞት በኩል የተፈጸመ ነው። የ1 ቆሮ 11፥25 ማብ ይመ።

22፥25 *በጎ አድራጊዎች*፤ በግብፅ፣ በሶርያና በሮም ለነበሩ ገዥዎች የሚሰጥ የክብር፣ የማዕረግ ስም ሲሆን፣ አብዛኛውን ጊዜ ይህ ማዕረግ ከገዢዎቹ ተግባር ጋር አይገናኝም።

22፥26 *እንደ አገልጋይ ይሁን*፤ የአገልጋይነት ባሕርይ ያለው መሪ መሆን አስፈላጊ እንደ ሆነ ኢየሱስ አስተምሮአል፤ እርአያም ሆኖ አሳይቶአል፤ እንዲህ ያለው ባሕርይ ያን ጊዜም ሆነ ዛሬ የለም።

22፥28 *በመከራዬ*፤ የገጠመውን ፈተና (ከ4፥13 ጋር ያነጻጽሩ)፣ መከራና (9፥58) ተቃውሞ (ዮሐ 1፥11) ያጠቃልላል።

22፥29 *በመንግሥቴ እሾማችኋለሁ*፤ ዐውደ ምንባቡ (ቍ30)፣ ይህ መንግሥት ወደፊት የሚመጣው መሆኑን ያመለክታል (የ4፥43፤ የማቴ 3፥2 ማብ ይመ)።

30ይኸውም በመንግሥቴ ከማእዴ እንድት በሉና እንድትጠጡ ደግሞም በዙፋን ላይ ተቀምጣችሁ በዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል ነገድ ላይ እንድትፈርዱ ነው።"

31ደግሞም ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ "ስምዖን፣ ስምዖን ሆይ፤ እነሆ፣ ሰይጣን እንደ ስንዴ ሊያበጥራችሁ ለመነ፤ 32እኔ ግን እምነትህ እንዳይጠፋ ስለ አንተ ጸለይሁ፤ አንተም በተመለስህ ጊዜ ወንድሞችህን አበርታ።"

33ስምዖንም፣ "ጌታ ሆይ፤ እኔ ከአንተ ጋር ወህኒ ለመውረድም፣ ለመሞትም ዝግጁ ነኝ" አለው።

34ኢየሱስም፣ "ጴጥሮስ ሆይ፤ ዛሬ ዶሮ ሳይጮኽ፣ አላውቀውም ብለህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ እልሃለሁ" አለው።

35ከዚያም ኢየሱስ፣ "ያለ ኰረጆ፣ ያለ ከረጢትና ያለ ጫማ በላክኋችሁ ጊዜ የጐደለባችሁ ነገር ነበርን?" ብሎ ጠየቃቸው።

እነርሱም፣ "ምንም አልጐደለብንም" አሉ።

36እርሱም እንዲህ አላቸው፤ "አሁን ግን ኰረጆም፣ ከረጢትም ያለው ሰው ይያዝ፤ ሰይፍ የሌለውም ልብሱን ሸጦ ይግዛ። 37እላችኋለሁና፤ 'ከዐመፀኞች ጋር ተቈጠረ' ተብሎ የተጻፈው በእኔ መፈጸም አለበት፤ ስለ እኔ የተጻፈው ፍጻሜው በእርግጥ ደርሶአል።"

38ደቀ መዛሙርቱም፣ "ጌታ ሆይ፤ እነሆ፤ ሁለት ሰይፎች እዚህ አሉ" አሉት።

እርሱም፣ "ይበቃል" አላቸው።

## ኢየሱስ በደብረ ዘይት ተራራ ጸለየ

2፥40-46 ተጓ ምብ – ማቴ 26 ፥36-46፤ ማር 14፥32-42

39ኢየሱስ እንደ ልማዱ ወጥቶ ወደ ደብረ ዘይት ተራራ ሄደ፤ ደቀ መዛሙርቱም ተከተሉት። 40እዚያም በደረሱ ጊዜ፣ "ወደ ፈተና እንዳትገቡ ጸልዩ" አላቸው። 41ከእነርሱም የድንጋይ ውርወራ ያህል ርቆ ተንበርክኮ ጸለየ፤ 42እንዲህም አለ፤ አባት ሆይ፤ ፈቃድህ ከሆነ፣ ይህችን ጽዋ ከእኔ ውሰድ፤ ነገር ግን የእኔ ፈቃድ ሳይሆን የአንተ ፈቃድ ይፈጸም።" 43መልአክም ከሰማይ ተገልጦለት አበረታታው። 44እጅግ ተጨንቆም በብርቱ ይጸልይ ነበር፤ ላቡም እንደ ደም ነጠብጣብ ወደ ምድር[a] ይፈስ ነበር።

45ከጸሎትም ተነሥቶ ወደ ደቀ መዛሙርቱ መጣ፤ እነርሱም ከሐዘን የተነሣ ተኝተው አገኛቸውና፣ 46"ለምን ትተኛላችሁ? ወደ ፈተና እንዳትገቡ ተነሥታችሁ ጸልዩ" አላቸው።

## ኢየሱስ ተያዘ

22፥47-53 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥47-56፤ ማር 14፥43-50፤ ዮሐ 18፥3-11

47እርሱም ገና እየተነጋገረ ሳለ፣ ብዙ ሰዎች መጡ፤ ከዐሥራ ሁለቱ አንዱ ይሁዳ የተባለውም ሰው ይመራቸው ነበር፤ ሊስመውም ወደ ኢየሱስ ተጠጋ። 48ኢየሱስ ግን፣ "ይሁዳ ሆይ፤ የሰውን ልጅ በመሳም አሳልፈህ ትሰጣለህን?" አለው።

49በኢየሱስ ዙሪያ የነበሩ ሰዎችም ሁኔታውን ተመልክተው "ጌታ ሆይ፤ በሰይፍ እንምታቸውን?" አሉት። 50ከእነርሱም አንዱ የሊቀ ካህናቱን አገልጋይ መትቶ ቀኝ ጆሮውን ቈረጠው።

51ኢየሱስ ግን፣ "ተው! እዚህ ድረስም ፍቀዱ" አለ፤ የሰውየውንም ጆሮ ዳስ ፈወሰው።

52ከዚያም ኢየሱስ ሊይዙት የመጡትን የካህናት አለቆች፣ የቤተ መቅደስ ሹሞችና

[a]44 አንዳንድ የጥንት ቅጆች ቍጥር 43 እና 44 የላቸውም

28፤ ሉቃ14፥15
22፥31 ኢዮ1፥6-12፤ አሞ9፥9
22፥32 ዮሐ17፥9:15፤ ዮሐ21፥15-17
22፥33 ዮሐ11፥16
22፥35 ማቴ10፥9:10፤ ሉቃ 9፥3፤10፥4
22፥37 ኢሳ53፥12
22፥39 ማቴ21፥1፤ ሉቃ21፥37
22፥40 ማቴ6፥13
22፥41 ሉቃ18፥11
22፥42 ማቴ20፥22፤ 26፥39
22፥43 ማቴ4፥11፤ ማር1፥13
22፥46 ቍ40
22፥49 ቍ38
22፥52 ቍ4

22፥30 *በዙፋን ላይ ተቀምጣችሁ፤* የኢየሱስን መከራ ተካፋዮች እንደ ነበሩ ሁሉ፣ በመንግሥቱም ተካፋዮች ይሆናሉ (2ጢሞ 2፥12)። *ዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል ነገድ፤* የማቴ 19፥28 ማብ ይመ። *እንድትፈርዱ፤* መሪ ወይም ገዢ መሆን ማለት ነው።

22፥31 *ሊያበጥራችሁ፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ። ሰይጣን፣ በደቀ መዛሙርቱ ላይ መንፈሳዊ ውድቀት ለማድረስ ሊፈትናቸው ፈለገ።

22፥36 *ኰረጆም... ከረጢትም፤* ቀደም ሲል ከተሰጠው መመሪያ ጋር ያነጻጽሩ (9፥3፤ 10፥4)። እስከ አሁን ይኖሩ የነበሩት የሚደረግላቸውን ልግስና ተስፋ በማድረግ ነበር፤ ወደፊት የሚመጣው ተቃውሞ ግን የራሳቸውን ኑሮ የመምራት ኀላፊነት እንዲኖራቸው ያደርጋል። *ይግዛ፤* ወደፊት ስለሚመጣው አስከፊ ጊዜ የማያስጠንቅቅ ተለዋጭ ዘይቤ ነው። ጳውሎስ፣ ሰይፍ ለታጠቀው ለቄሳር ይግባኝ እንዳለ ሁሉ (ሐሥ 25፥11፤ ሮሜ 13፥4)፣ መከላከያና ጥበቃ ያስፈልጋቸዋል።

22፥37 *ከዐመፀኞች ጋር ተቈጠረ፤* በቅዱሳት መጻሕፍት የተነገረው ትንቢት ይፈጸም ዘንድ፣ ኢየሱስ እንደ ወንጀለኛ ተቈጥሮ መያዝ ነበረበት፤ ከዚህ የተነሳም የእርሱ ተከታዮች የሆኑት ደቀ መዛሙርት አደገኛ ሁኔታ በፊታቸው ተደቅኖባቸው ነበር።

22፥38 *ሁለት ሰይፎች... "ይበቃል"፤* ኢየሱስ የተናገረውን ደቀ መዛሙርቱ ቃል በቃል እንደ ተረዱት አስተውሎ "ይበቃል" በሚል ምፀታዊ አነጋገር የጀመረውን ንግግር ደመደመ፤ ብዙ ሳይቈይም ጴጥሮስ ሰይፍ በመምዘዙ ገሠጸው (ቍ 50)።

22፥39 *ደብረ ዘይት ተራራ፤* 21፥37፤ዮሐ 18፥2 ይመ። ማቴዎስ ለይቶ 'ጌቴሴማኒ' ሲል (ማቴ 26፥36)፣ ዮሐንስ ደግሞ 'የአትክልት ቦታ' ብሎታል (ዮሐ 18፥1)፣ ቦታው በደብረ ዘይት ተራራ ተዳፋት ላይ የሚገኝ ሳይሆን አይቀርም።

22፥40 *ፈተና፤* በቍ 28፣38 ላይ እንደ ተጠቀሰው ዐይነት እምነታቸውን ሊያላላ የሚደርስ ከባድ ፈተና ነው።

22፥42 *ይህችን ጽዋ፤* የመከራ ጽዋ ማለት ነው (ማቴ 20፥22-23፤ ከኢሳ 51፥17፤ ከሕዝ 23፥33 ጋር ያነጻጽሩ)፤ የማር 14፥36 ማብ ይመ።

22፥43 *መልአክም፤* በጾመ ጊዜና በፈተናው መጨረሻ ላይ ኢየሱስን መላእክት እንዳገለገሉት ማቴዎስና ማርቆስ ጽፈዋል (ማቴ 4፥11፤ ማር 1፥13)፤ ሉቃስ ግን ይህን አልጻፈም፤ በሌላ በኩል ደግሞ የሚያጽናናው መልአክ በአጠገቡ እንደ ነበር ሉቃስ ሲጽፍ፣ ሌሎቹ ወንጌላውያን ግን አልጻፉም።

22፥44 *እንደ ደም፤* ጌታ ሲጸልይ ላቡ ደም መምሰሉ፣ የሚቀበለው መከራ ምን ያህል ከባድ እንደ ሆነ ያመለክታል።

22፥47 *ብዙ ሰዎች መጡ፤* ከካህናት አለቆች፣ ከሽማግሌዎችና (ማቴ 26፥47) ከጸሐፍት (ማር 14፥43) የተላኩ ናቸው፤ እነርሱም ሰይፍና ዱላ ይዘው ነበር፤ ከእነዚህም ጋር አንድ የወታደር ቡድንና የአይሁድ ሹማምንት ነበሩ (ቍ 52፤ ዮሐ 18፥3)። *ሊስመው፤* ባለ ሥልጣናቱ ኢየሱስን ለይተው እንዲያውቁት በቅድሚያ የተሰጠ ምልክት ነው (ማቴ 26፥48)፤ ይህ ሆኖ ሳለ ኢየሱስ በግልጽ ራሱን አሳውቋቸው ስለ ነበር (ዮሐ 18፥5)፣ ምልክቱ አስፈላጊ አልነበረም፤ ቢሆንም ይሁዳ ያቀደውን ከመፈጸም ወደ ኋላ አላለም።

22፥50 *የሊቀ ካህናቱን አገልጋይ፤* የዚህ ሰው ስም ማልኮስ ነው፣ ጆሮውን የቈረጠውም ጴጥሮስ ነበር (ዮሐ 18፥10)።

22፥51 *ፈወሰው፤* ኢየሱስ፣ ደቀ መዝሙሩ የፈጸመውን ስሕተት አስተካከለ፤ ማልኮስ ፈውስን የተቀበለው እምነት ስለ ነበረው አይደለም፤ የጴጥሮስን ስሕተት ኢየሱስ ችላ ብሎ ያላለፈው፣ ድርጊቱ ካስተማረው ትምህርት ጋር የማይጣጣም በመሆኑ ነው።

ሽማግሌዎችን እንዲህ አላቸው፤ “ወንበዴ እንደሚይዝ ሰው፣ ሰይፍና ቈመጥ ይዛችሁ ወጣችሁን? [53]በየዕለቱ በቤተ መቅደስ ከእ ናንተ ጋር በነበርሁ ጊዜ እጃችሁን አላነሣ ችሁብኝም፤ ይህ ግን ጨለማ የነገሠበት ጊዜ ያችሁ ነው።”

## ጴጥሮስ ኢየሱስን ካደ

22፥55-62 ተጓ ምብ – ማቴ 26፥69-75፤ ማር 14፥66-72፤ ዮሐ 18፥16-18፡ 25-27

[54]ከዚህ በኋላ ኢየሱስን ይዘው ወሰዱት፤ ወደ ሊቀ ካህናቱም ግቢ አስገቡት፤ ጴጥሮ ስም በርቀት ይከተለው ነበር። [55]ሰዎቹ በሊቀ ካህናቱ ግቢ ውስጥ እሳት አንድደው በአንድነት ተቀምጠው ሳለ፣ ጴጥሮስም ከእነርሱ ጋር ተቀምጦ ነበር። [56]አንዲት የቤት ሠራተ ኛም ጴጥሮስ እሳቱ አጠገብ ተቀምጦ አየ ችውና ትኵር ብላ በመመልከት፣ “ይህ ሰው ደግሞ ከእርሱ ጋር ነበረ” አለች።

[57]እርሱ ግን፣ “አንቺ ሴት፤ እኔ ዐላውቀ ውም” ብሎ ካደ።

[58]ከጥቂት ጊዜ በኋላም አንድ ሌላ ሰው አይቶት፣ “አንተም ደግሞ ከእነርሱ አንዱ ነህ” አለው።

ጴጥሮስ ግን፣ “አንተ ሰው፤ እኔ አይደለሁም” አለ።

[59]አንድ ሰዓት ያህል ቈይቶም፣ ሌላ ሰው በእርግጠኝነት፣ “ይህ ሰው ገሊላዊ ስለ ሆነ ያለ ጥርጥር ከእርሱ ጋር ነበረ” አለ።

[60]ጴጥሮስ ግን፣ “አንተ ሰው፤ የምትለውን እኔ አላውቅም” አለ፤ ይህንም ተናግሮ ገና ሳይጨርስ ዶሮ ጮኸ። [61]ጌታም መለስ ብሎ ጴጥሮስን ተመለከተው፤ ጴጥሮስም፣ “ዛሬ ዶሮ ሳይጮኽ ሦስት ጊዜ ትክደ ኛለህ” ብሎ ጌታ የተናገረው ቃል ትዝ አለው። [62]ጴጥሮስም ወደ ውጭ ወጥቶ ምርር ብሎ አለቀሰ።

22፥53 ማቴ8፥12፤ 26፥55፤ ዮሐ1፥5፤ 3፥20፤12፥27
22፥54 ማቴ26፥57፡58፤ማር14፥53፡54፤ ዮሐ18፥15
22፥59 ሉቃ23፥6
22፥61 ቍ34፤ ሉቃ7፥13
22፥65 ማቴ16፥21
22፥66 ማቴ5፥22፤ 27፥1፤ ማር15፥1
22፥68 ሉቃ20-8
22፥69 ማር16፥19
22፥70 ማቴ4፥3፤ 27፥11፤ ሉቃ23፥3
23፥1 ማቴ27፥2
23፥2 ቍ14፤ ሉቃ20፥22፤ ዮሐ119፥12

## ወታደሮች በኢየሱስ ላይ አፌዙበት

22፥63-65 ተጓ ምብ - ማቴ 26፥67፡68፤ ማር 14፥65፤ ዮሐ 18፥22፡23

[63]ኢየሱስን አስረው ይጠብቁት የነበሩት ሰዎችም ያፌዙበትና ይመቱት ጀመር፤ [64]ዐይኑንም ሸፍነው፣ “እስቲ ትንቢት ተና ገር፤ የመታህ ማነው? እያሉ ይጠይቁት ነበር። [65]ሌላም ብዙ የስድብ ቃል እየተና ገሩ ያቃልሉት ነበር።

## ኢየሱስ በጲላጦስና በሄሮድስ ፊት

22፥67-71 ተጓ ምብ –ማቴ 26፥63-66፤ ማር 14፥61-63፤ ዮሐ 18፥19-21
23፥2፡3 ተጓ ምብ –ማቴ 27፥11-14፤ ማር15፥2-5፤ ዮሐ 18፥29-37
23፥18-25 ተጓ ምብ –ማቴ 27፥15-26፤ ማር 15፥6-15፤ ዮሐ 18፥39-19፥16

[66]በነጋም ጊዜ፣ የሕዝብ ሽማግሌዎች፣ የካህናት አለቆችና ጸሐፍት ተሰበሰቡ፤ ኢየሱስንም በሸንጎአቸው ፊት አቀረቡት። [67]እነርሱም፣ “አንተ ክርስቶስ° ነህን? እስቲ ንገረን” አሉት።

ኢየሱስም እንዲህ አላቸው፤ “ብነግራችሁ አታምኑኝም፤ [68]ብጠይቃችሁም አትመል ሱም። [69]ነገር ግን ከአሁን ጀምሮ የሰው ልጅ በእግዚአብሔር ኀይል ቀኝ ይቀመጣል።”

[70]በዚህ ጊዜ ሁሉም፣ “ታዲያ፣ አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ነህን?” አሉት።

እርሱም፣ “መሆኔን እኮ እናንተው ተናገ ራችሁት” አላቸው።

[71]እነርሱም፣ “ከእንግዲህ ሌላ ምስክር ምን ያስፈልገናል? ራሳችን ከገዛ አንደበቱ ሰምተናልና” አሉ።

**23** በዚያ የተሰበሰቡት በሙሉ ተነሥ ተው ኢየሱስን ወደ ጲላጦስ ወሰ ዱት፤ [2]እንዲህም እያሉ ይከሱት ጀመር፤ “ይህ ሰው ሕዝባችንን ሲያስት፣ ለቄሳር ግብር እንዳይከፈል ሲከለክል፣ ደግሞም፣ ‘እኔ ክርስቶስ" ንጉሥ ነኝ’ ሲል አገኘነው።”

[3]ጲላጦስም፣ “አንተ የአይሁድ ንጉሥ ነህን? ” ብሎ ጠየቀው።

°67 ወይም መሲሕ
"2 ወይም መሲሕ፤ እንዲሁም ቍ 35 እና 39 ይመ

22፥53 *ጊዜያችሁ ነው፤* የኢየሱስ ጠላቶች ኢየሱስን በቍ ጥጥራቸው ሥር ያደርጉ ዘንድ የተመደበላቸው ጊዜና የጨለማ (ክፉ) ኀይላት የእግዚአብሔርን ዕቅድ ለማክሸፍ የሚፍጨረጨሩ በት ወቅት ነበር።

22፥54 *ሊቀ ካህናቱም ግቢ፤* የ3፥2፤ ማር 14፥53፤ 15፥15 ማብ ይመ።

22፥59 *ይህ ሰው ገሊላዊ ስለ ሆነ፤* ማንነቱ የታወቀው በአነጋገሩና (ማቴ 26፥73) የሊቀ ካህናቱ ባሪያ በሆነው በማልኮስ ዘመድ በመሆኑ ነበር (ዮሐ 18፥26)።

22፥61 *ጌታም... ጴጥሮስን ተመለከተው፤* ኢየሱስ ጴጥሮ ስን ዘወር ብሎ የተመለከተው፣ ጴጥሮስም በአጥር ግቢው ውስጥ ስለ ነበር ነው። ቀያፋ ዘንድ ቀርቦ ከተጠየቀ በኋላ፣ ወደ አይ ሁድ የፍርድ ሸንጎ በሚወሰድበት ጊዜ ሳይሆን አይቀርም። *ጴጥ ሮስም... ትዝ አለው፤* ትዝ ያለው ኢየሱስ የተናገረው ቃል ነው (ቍ 34)።

22፥66 *በነጋም ጊዜ፤* መላው የአይሁድ ሸንጎ፣ የሞት ፍርድ ለመፍረድ ችሎት የሚቀመጠው በምሽት ሳይሆን ቀን ብቻ ነው።

22፥67 *ክርስቶስ ነህን?* ይህ ጥያቄ ከዚህ ቀጥሎ ከቀረበው “አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ነህን” (ቍ 70) ከሚለው ጋር የተያያዘ ነው።

22፥71 *ራሳችን ... ሰምተናልና፤* ኢየሱስ ለሰጣቸው መልስ ያሳዩት ሁኔታ፣ መልሱ የማያሻማ አወንታዊ መሆኑን ነው። ማርቆስ፣ “እኔ ነኝ” ያለውን ጽፎአል (ማር 14፥62)፤ እውነተኛ መሢሕ ሳይሆን “መሢሕ ነኝ” እንዲሁም “የእግዚአብሔር ልጅ ነኝ” ማለት እግዚአብሔር እንደ መሳደብ ይቈጠር ነበር (የማር 14፥64 ማብ ይመ)።

23፥1 *የተሰበሰቡት በሙሉ፤* ሊነጋጋ ሲል (22፥66) የተሰበ ሰቡት የአይሁድ ሸንጎ (ማቴ 26፥59፤27፥1) አባላት ማለት ነው። *ወደ ጲላጦስ ወሰዱት፤* የማቴ 27፥2 ማብ ይመ። *ጲላጦስ፤* የማር 15፥1 ማብ ይመ። ይህ ሮማዊ ገዥ፣ ዋና የሥልጣን መንበሩ ቂሣርያ ሲሆን፣ በዓሉን ለማክበር በፋሲካ ሰሞን የሚሰበሰበውን አያሌ የአይሁድ ሕዝብ ሊቀሰቅስ የሚችለውን ዐመፅ ለመቈጣጠር በኢየሩሳሌም ይገኝ ነበር።

23፥2 *ሕዝባችንን ሲያስት፤* ብዙ ሕዝብ ኢየሱስን ተከት ሎታል፤ ይሁን እንጂ ይህን ሕዝብ ወደ ተሳሳተ መንገድ አልመ ራም፤ ወይም በሮም መንግሥት ላይ እንዲያምፁ አላደረገም። *ግብር እንዳይከፈል ሲከለክል፤* በኢየሱስ ላይ የቀረበ የሐሰት ክስ ነበር (20፥25 ይመ)። እኔ ክርስቶስ ንጉሥ ነኝ ሲል፤ ኢየሱስ ‘መሲሕ ነኝ’ ብሎአል፤ ሆኖም የሮምን መንግሥት የሚቀናቀን ፖለ ቲካዊ ወይም ወታደራዊ ንጉሥ አልነበረም።

1 በእግዚአብሔር ፈቃድ የክርስቶስ ኢየሱስ ሐዋርያ እንዲሆን ከተጠራው ከጳውሎስ፣ ከወንድማችንም ከሶስቴንስ፤

2 በቆሮንቶስ ላለችው የእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን፤ በክርስቶስ ኢየሱስ ተቀድሰው፣ የእነርሱና የእኛ ጌታ የሆነውን የጌታችንን የኢየሱስ ክርስቶስን ስም በየስፍራው ሆነው ከሚጠሩት ሁሉ ጋር ቅዱሳን ለመሆን ለተጠሩት፤

3 ከእግዚአብሔር ከአባታችን፣ ከጌታም ከኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋና ሰላም ለእናንተ ይሁን።

## ምስጋና

4 በክርስቶስ ኢየሱስ ስለ ተሰጣችሁ ጸጋ ዘወትር ስለ እናንተ እግዚአብሔርን አመሰግናለሁ። 5 ምክንያቱም በማናቸውም ነገር ይኸውም በንግግር ሁሉ፣ በዕውቀትም ሁሉ በእርሱ በልጽጋችኋል፤ 6 ስለ ክርስቶስ የመሰከርንላችሁም በእናንተ ዘንድ ጸንቶአል። 7 ስለዚህ የጌታችንን የኢየሱስ ክርስቶስን መገለጥ በጕጕት በመጠባበቅ ላይ ሳላችሁ፣ ማንኛውም መንፈሳዊ ስጦታ አይጐድልባችሁም። 8 በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ቀን ያለ ነቀፋ እንድትገኙ እርሱ እስከ መጨረሻው ድረስ አጽንቶ ይጠብቃችኋል። 9 ወደ ልጁ፣ ወደ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ኅብረት የጠራችሁ እግዚአብሔር የታመነ ነው።

## በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ የተከሠተ መለያየት

10 ወንድሞች ሆይ፤ በመካከላችሁ መለያየት እንዳይኖር፣ አንድ ልብ፣ አንድ ሐሳብ እንዲኖራችሁ፤ እርስ በርሳችሁም እንድትስማሙ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም እለምናችኋለሁ። 11 ወንድሞች ሆይ፤ በመካከላችሁ ክርክር እንዳለ ከቀሎዔ ቤተ ሰብ ሰምቻለሁ፤ 12 ነገሩም እንዲህ ነው፤ ከእናንተ አንዱ፣ "እኔ የጳውሎስ ነኝ" ሲል፣ ሌላው፣ "እኔ የአጵሎስ ነኝ" ይላል፤ ደግሞም አንዱ፣ "እኔ የኬፋ[ሀ] ነኝ" ሲል፣ ሌላው ደግሞ፣ "እኔስ የክርስቶስ ነኝ" ይላል።

13 ለመሆኑ ክርስቶስ ተከፍሎአልን? ጳውሎስስ ለእናንተ ተሰቅሎአልን? ወይስ በጳውሎስ[ለ] ስም ተጠምቃችኋልን? 14 ከቀርስጶስና ከጋይዮስ በስተቀር ከእናንተ ማንንም ስላላጠመቅሁ እግዚአብሔርን አመሰግናለሁ፤ 15 ስለዚህ በስሜ መጠመቁን የሚናገር ማንም የለም። 16 እርግጥ የእስጢፋኖስን ቤተ ሰው አጥምቄአለሁ፤ ከእነዚህ ሌላ ግን ማጥመቄ ትዝ አይለኝም። 17 ክርስቶስ የላከኝ ወንጌልን እንድሰብክ እንጂ እንዳጠምቅ አይደለም፤ የክርስቶስም መስቀል ከንቱ እንዳይሆን፣ በሰዎች የንግግር ጥበብ አልሰብክም።

## ክርስቶስ የእግዚአብሔር ኀይልና ጥበብ

18 የመስቀሉ ቃል ለሚጠፉ ሞኝነት ነው፤ ለእኛ

1፥1 ሐሥ18፥17፤ ሮሜ1፥1፤2ቆሮ1፥1፤ ኤፌ1፥1፤2ጢሞ1፥1
1፥2 ሐሥ2፥21፤ 18፥1፤ ሮሜ1፥7፤ 1ቆሮ10፥32
1፥3 ሮሜ1፥7
1፥4 ሮሜ1፥8
1፥5 2ቆሮ8፥7፤ 9፥11
1፥6 2ተሰ1፥10፤ 1ጢሞ2፥6፤ራእ1፥2
1፥7 ማቴ16፥27፤ ሉቃ17፥30፤ ሮሜ1፥11፤1ቆሮ12፥1-31፤1ተሰ1፥10፤ 2፥19፤ቲቶ2፥13፤ ያዕ5፥7፡8፤1ጴጥ1፥13፤ 2ጴጥ3፥12፤ራእ1፥7
1፥8 አሞ5፥18፤ 1ቆሮ5፥5፤ፊል1፥6፡ 10፤2፥16፤ 1ተሰ3፥13፤5፥2
1፥9 ዘዳ7፥9፤ ኢሳ49፥7፤ሮሜ8፥28፤ 1ቆሮ10፥13፤ 1ተሰ5፥24፤2ተሰ3፥3፤ 2ጢሞ2፥13፤ ዕብ10፥23፤ 11፥11፤1ዮሐ1፥3
1፥10 ሮሜ7፥1፤ 15፥5፤1ቆሮ11፥18
1፥11 ሐሥ11፥14
1፥12 ዮሐ1፥42፤ ሐሥ18፥24፤ 1ቆሮ3፥4:22፤9፥5
1፥13 ማቴ28፥19
1፥14 ሐሥ18፥8፤ 19፥29
1፥16 ሐሥ11፥14፤1ቆሮ16፥15 1፥17 ዮሐ4፥2፤ሐሥ2፥38፤ 1ቆሮ2፥1:4:13፤1፥18 ቍ21:23: 24:25፤ሐሥ2፥47፤ሮሜ1፥16፤ 1ቆሮ2፥14፤2ቆሮ2፥15፤4፥3፤2ተሰ2፥10

ሀ12 ጴጥሮስ ማለት ነው
ለ13 ወይም *ወደ ጳውሎስ፤* እንዲሁም ቍ 15 ይመ

1፥1 *የክርስቶስ ኢየሱስ ሐዋርያ፡* የማር 6፥30፤ የዕብ 3፥1 ማብ ይመ። ጳውሎስ ይህን መጠሪያ በመልእክቶቹ ሁሉ ለራሱ አውሎት ይገኛል (ከፊልጵስዩስ፣ ከ1ኛና ከ2ኛ ተሰሎንቄ እንዲሁም ከፊልሞና በቀር)፤ ይህንም ያደረገው ተቀባይነት ያጣው ሥልጣኑ እንዲረጋገጥለት ነበር (ም 9 እና 2ቆሮ 11 ይመ)። ሥልጣኑንም፣ "በእግዚአብሔር ፈቃድ ... ከተጠራው" በማለት ይበልጥ ተቀባይነት እንዲያገኝ ያደርጋል። *ሶስቴንስ፡* ግሪኮች የደበደቡት፣ በቆሮንቶስ የነበረው የምኵራብ አለቃ ሳይሆን አይቀርም፤ (ሐሥ 18፥17)። በእርግጥ እርሱ ከሆነ፣ ጳውሎስ በቆሮንቶስ በሰበከበት ወቅት (ሐሥ 18፥18)፣ ወይም አጵሎስ በቆሮንቶስ ባገለገለበት ጊዜ (ሐሥ 19፥1) አምኖ ሊሆን ይችላል። *ጳውሎስ፡* በግሪኮች ልማድ ደብዳቤ የሚጀምረው በጸሓፊው ስም ነበር። ስለ ጳውሎስ ይበልጥ ለማወቅ የሐሥ 9፥1፤ የፊል 3፥4-14 ማብ ይመ።

1፥2 *የእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን፡* ይህን ሐረግ የተጠቀመበት ጳውሎስ ብቻ ሲሆን፣ የሚገኘውም በሐሥ 20፥28፤ እዚህ ላይና በ2ቆሮ 1፥1 ላይ ነው። በብሉይ ኪዳን ከዚህ ሐረግ ጋር ተተካካይ የሚሆነው፣ "የእግዚአብሔር ጉባኤ" የሚለው ነው (ዘዳ 23፥1፤ ይመ፤ እንዲሁም ዘኍ 16፥3፤ 20፥4፤ 1ዜና 28፥8 ይመ)። *ተቀድሰው፤* ለጌታ የተለዩ ወይም የተቀደሱ ማለት ሲሆን፣ የሚቀደሱትም ፦ (1) ክርስቶስ በመስቀል ላይ ያስገኘውን ስርየት በእምነት በመቀበል (ወዲያው የሚሆን)፤ (2) መንፈስ ቅዱስ በክርስቲያኖች ሕይወት ውስጥ በሚሠራው ሥራ አማካይነት (በሂደት የሚሆን) ነው።

1፥3 *ጸጋና ሰላም፤* የዮና 4፥2፤ የዮሐ 14፥27፤ 20፥19፤ የገላ 1፥3፤ የኤፌ 1፥2 ማብ ይመ።

1፥4 *አመሰግናለሁ፤* ሮሜ 1፥8 ይመ።

1፥5 *በንግግር ሁሉ፣ በዕውቀትም ሁሉ፡* እነዚህ የመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች ናቸው (12፥8 ይመ፤ እንዲሁም 2ቆሮ 8፥7 ይመ)።

1፥6 *ጸንቶአል፤* ጳውሎስ ስለ ክርስቶስ የሰበከው ቃል በቆሮንቶስ ሰዎች ዘንድ ተቀባይነት ያገኘ ሲሆን፣ የተሰበከላቸውንም ቃል መቀበላቸው በሕይወታቸው ታይቶአል።

1፥7 *ማንኛውም መንፈሳዊ ስጦታ፤* ከም 12-14 ላይ የተጠቀሱትን ስጦታዎች ሳይሆን አይቀርም፤ በእነዚህ ምዕራፎች መሠረት፣ መንፈሳዊ ስጦታ ሲባል የመንፈስ ቅዱስ በአማኞች መገለጥ ሲሆን፣ ይኸውም አንድ ክርስቲያን ቤተ ክርስቲያንን በሚያስፈልጋት ሁሉ እንዲያገለግል ያስችለዋል (12፥7-11፤ 14፥3:12:17)። "*መንፈሳዊ ስጦታ*" ለሚለው ሐረግ የገባው የግሪኩ ቃል፣ ስጦታው የጸጋ ስጦታ መሆኑን በአጽንዖት ያሳያል።

1፥8 *በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ቀን፤* ክርስቶስ ተመልሶ የሚመጣበትን ቀን ማለት ነው (ቍ 7፤ ፊል 1፥6)። *እርሱ፤* እግዚአብሔር አብን ነው። *መጨረሻው፤* ክርስቶስ ዳግም የሚመጣበትን ዘመን ማለት ነው።

1፥9 *እግዚአብሔር የታመነ ነው፤* የገባውን ቃል ተስፋ ስለሚጠብቅ፣ ሊታመን ይገባዋል (1ተሰ 5፥24)፤ ይህም አማኞችን፣ "እስከ መጨረሻው ድረስ አጽንቶ" ስለሚጠብቅ ነው (ቍ 8)።

1፥10 *ወንድሞች፤* በክርስቶስ ኢየሱስ የሚያምኑ ሁሉ እንደ ሥጋ ወንድምና እኅት የተሳሰሩ መሆናቸውን ያመለክታል። እዚህ ላይ ጳውሎስ፣ "ወንድሞች" ሲል፣ ወንዶችንና ሴቶችን ነው (16፥20፤ ሮሜ 16፥3:6-7:12-13:15 ይመ)።

1፥11 *ክርክር፤* ገላ 5፥19፤ ያዕ 4፥12 ይመ።

1፥12 *አጵሎስ፤* በቆሮንቶስ ፍሬያማ አገልግሎት የነበረው ሰው ነው፤ (ሐሥ 18፥24-28፤ 19፥1 ይመ)። *ኬፋ፤* የጴጥሮስ ሌላው ስሙም ነው፤ የዮሐ 1፥42 ማብ ይመ፤ በቆሮንቶስ ጴጥሮስን የተከተሉት ከአይሁድ ወገን የሆኑ ክርስቲያኖች እንደ ነበሩ ይገመታል።

1፥13 *ክርስቶስ ተከፍሎአልን?* 12፥12-13 ይመ። *በጳውሎስ ስም፤* "በ - ስም" መጠመቅ ማለት የዚያ ሰው ተከታይ ወይም ለዚያ ሰው ቅርበት ያለው ማለት ነው።

1፥16 *እስጢፋኖስ፡* 16፥15:17 ይመ። *ቤተ ሰብ፤* ከዚህ ሌላ የተጠመቁት ቤተ ሰዎች የቆርኔሌዎስ (ሐሥ 10፥24:48)፣ የልድያ (ሐሥ 16፥15)፣ እንዲሁም የፊልጵስዩስ የወህኒ ቤት ጠባቂ ናቸው (ሐሥ 16፥33-34)። "ቤተ ሰው" ሲባል የቤተ ሰብ አባላትን፣ የቤት አገልጋዮችን ወይም በቤት ውስጥ የዋለ ያደረውን ሰው ሁሉ ያመለክታል።

1፥17 *እንዳጠምቅ አይደለም፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ እግዚአብሔር ለይቶ የሰጠውን የማስተማር ኀላፊነት ለማመልከት እንጂ፣ ጥምቀትን ማቃለሉ አይደለም። ጌታ ኢየሱስና (ዮሐ 4፥2) ሐዋርያው ጴጥሮስም (ሐሥ 10፥48)፣ ሌሎች እንዲያጠምቁ አደረጉ እንጂ እነርሱ ራሳቸው አላጠመቁም። *በሰዎች የንግግር ጥበብ፡* የጳውሎስ ተልዕኮ ሰዎችን በረቀቀ የንግግር ችሎታ እያግባባ ወንጌልን

ለምንድነው ግን የእግዚአብሔር ኀይል ነው፤ [19]እንዲህ ተብሎ ተጽፎአልና፤

"የጥበበኞችን ጥበብ አጠፋለሁ፤
የዐዋቂዎችንም ዕውቀት ከንቱ አደርጋለሁ።"

[20]ጠቢብ የት አለ? ሊቅስ የት አለ? የዘመኑስ ፈላስፋ የት አለ? እግዚአብሔር የዓለምን ጥበብ ሞኝነት አላደረገምን? [21]ከእግዚአብሔር ጥበብ የተነሣ ዓለም በገዛ ጥበብዋ እግዚአብሔርን ማወቅ ስላ ተሳናት፣ በስብከት ሞኝነት የሚያምኑትን ያድን ዘንድ የእግዚአብሔር በጎ ፈቃድ ሆኖአል። [22]መቼም አይሁድ ታምራዊ ምልክትን ይፈልጋሉ፤ የግሪክ ሰዎችም ጥበብን ይሻሉ፤ [23]እኛ ግን የተሰቀለውን ክርስቶስን እንሰብካለን፤ ይህም ለአይሁድ መሰናክል፣ ለአሕዛብ ደግሞ ሞኝነት ነው። [24]እግዚአብሔር ለጠራቸው ግን፣ አይሁድም ሆኑ ግሪኮች፣ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ኀይል፣ የእግዚአብሔርም ጥበብ ነው። [25]ምክንያቱም ከሰው ጥበብ ይልቅ የእግዚአብሔር ሞኝነት ይጠበባል፣ ከሰውም ብርታት ይልቅ የእግዚአብሔር ድካም ይበረታል።

[26]ወንድሞች ሆይ፤ በተጠራችሁ ጊዜ ምን እንደ ነበራችሁ እስቲ አስቡ። በሰው መስፈርት ከእናንተ ብዙዎቻችሁ ዐዋቂዎች አልነበራችሁም፤ ብዙዎቻችሁም ኀያላን አልነበራችሁም፤ ብዙዎቻችሁም ከትልቅ ቤተ ሰብ አልተወለዳችሁም። [27]ነገር ግን እግዚአብሔር ጥበበኞችን ያሳፍር ዘንድ የዓለምን ሞኝ ነገር መረጠ፤ እግዚአብሔር ብርቱዎችን ያሳፍር ዘንድ የዓለምን ደካማ ነገር መረጠ። [28]እግዚአብሔር የተከበረውን እንደሌለ ለማድረግ፣ በዚህ ዓለም ዝቅ ያለውንና የተናቀውን ነገር፣ ቦታም ያልተሰጠውን ነገር መረጠ፤ [29]ይኸውም ማንም ሰው በእርሱ ፊት እንዳይመካ ነው። [30]በክርስቶስ ኢየሱስ ለመሆን የበቃችሁት ከእርሱ የተነሣ ነው፤ እርሱ ከእግዚአብሔር ዘንድ ጥበባችን፣ ጽድቃችንና ቅድስናችን፣ ቤዛችንም ሆኖአል። [31]እንግዲህ፣ እንዲህ ተብሎ እንደ ተጻፈ ነው፤ "የሚመካ በጌታ ይመካ።"

1፥19 ኢሳ29፥14
1፥20 ቍ27፤ ኢዮ12፥17፤ኢሳ19፥11፡12፤44፥25፤ኤር8፥9፤ሮሜ 1፥22፤1ቆሮ2፥6፡8፡13፥18፡19፤2ቆሮ4፥4፤ገላ1፥4
1፥21 ቍ27፡28፤ሮሜ3፥22፤11፥14፤1ቆሮ6፥2፤11፥32
1፥22 ማቴ12፥38፤ዮሐ2፥11፤4፥48
1፥23 ቍ18፤ ሉቃ2፥34፤1ቆሮ2፥2፤ገላ3፥1
1፥24 ቍ18፡30፤ሮሜ 1፥16፤8፥28፤ቈላ2፥3
1፥25 ቍ18፤ 2ቆሮ13፥4
1፥26 ቍ20፤ ሮሜ8፥28
1፥27 ቍ20፤ ሮሜ1፥22፤ 1ቆሮ3፥18፡19፤ ያዕ2፥5
1፥28 ሮሜ4፥17
1፥29 ኤፌ2፥9
1፥30 ኤር23፥5፡6፤33፥16፤ሮሜ3፥24፤16፥3፤1ቆሮ1፥2፤ 2ቆሮ5፥21፤ፊል3፥9
1፥31 መዝ34፥2፤44፥8፤ኤር9፥23፡24፤ 2ቆሮ10፥17
2፥1 ቍ4፡13፤ 1ቆሮ1፥17 2፥2 1ቆሮ1፥23፤ገላ6፥14

# 2

ወንድሞች ሆይ፤ ወደ እናንተ በመጣሁ ጊዜ፣ የእግዚአብሔርን ምስጢር[ሐ] በረቀቀ የንግግር ችሎታ ወይም በላቀ ጥበብ ልገልጥላችሁ አልመጣሁም። [2]በመካከላችሁ ሳለሁ ኢየሱስ ክርስቶስን ያውም የተሰቀለውን፣ እርሱን ብቻ እንጂ ሌላ እንዳላውቅ ወስኜ ነበርና። [3]ወደ እናንተ የመጣሁት በድካምና በፍርሃት፣ እንዲሁም በብዙ መንቀጥቀጥ ነበር። [4]ቃሌም ስብከቴም የመንፈስን ኀይል በመግለጥ እንጂ፣ በሚያባብል የጥበብ ቃል አልነበረም፤ [5]ይኸውም እምነታችሁ በእግዚአብሔር ኀይል እንጂ በሰው ጥበብ ላይ እንዳይመሠረት ነው።

2፥3 ሐሥ18፥1-18፤1ቆሮ4፥10፤9፥22፤2ቆሮ7፥15፤11፥29፡30፤12፥5፡9፡10፤13፥9 2፥4 ቍ1፤ሮሜ15፥13 2፥5 2ቆሮ4፥7፤6፥7

[ሐ]1 አንዳንድ ቅጆች *ስለ እግዚአብሔር* ይላሉ

ማስተማር አልነበረም።

1፥19፤ ይህ ጥቅስ የተወሰደው ከኢሳ 29፥14 ሲሆን፣ በይሁዳ የሚገኙ፣ "ጠቢባን" የአሦር ንጉሥ ሰናክሬም በይሁዳ ላይ በዛተ ጊዜ፣ ከግብፅ ጋር ለማበር ጠቢባኑ ያወጡትን ዕቅድ እግዚአብሔር የነቀፈበት ነው። *ጥበበኞች፤* አሪስጠጣዲስ የተባለ ሊቅ፣ አንድ ሰው በቆሮንቶስ ከተማ በየአደባባዩ ጠቢባን ነኝ ባዮች እንደሚያጋጥሙትና እነዚህም ሰዎች በዚህ ዓለም ላለ ችግር ሁሉ የየራሳቸውን መፍትሔ ይሰጡ እንደነበር ተናግሮአል።

1፥20 *ጠቢብ፤* በጥቅሉ የአሕዛብን ፈላስፎች ሊሆን ይችላል። *ሊቅ፤* የአይሁድ ሕግ መምህራንን ሊሆን ይችላል (የማቴ 2፥4 ማብ ይመ)። *የዘመኑስ ፈላስፋ፤* የተንዛዛና የረቀቀ ክርክር የሚወዱ የግሪክን ሊቃውንት ሊሆን ይችላል። *እግዚአብሔር የዓለምን ጥበብ ሞኝነት አላደረገምን?* በሰው ብልኀት የተገኘ ዕውቀት በመጨረሻ ትርጕም የለሽ ይሆናል፤ ምክንያቱም እግዚአብሔርንና እርሱ የሰጠውን መገለጥ በትክክል አያገናዝብም።

1፥21 *ጥበብ … ሞኝነት፤* ኢየሱስ በሉቃ 10፥21 ላይ የተናገረው ቃል ከዚህ ጋር ተመሳሳይነት አለው። የዚህ ዓለም ጥበብ እግዚአብሔር የሚታወቅበት መንገድ እንዳይሆን የአምላክ ሐሳብ ነው። *በስብከት ሞኝነት፤* ስብከት ሞኝነት ነው ማለት ሳይሆን፣ "ክርስቶስ ተሰቀለ" የሚለው ትምህርት በዓለም ዐይን ሲታይ እንደ ሞኝነት ይቈጠራል ማለት ነው።

1፥22 *የግሪክ ሰዎችም ጥበብን ይሻሉ፤* በጥቅሉ የግሪክ ሰዎችን የሚመለከት ቢሆንም፣ በተለይ ደግሞ የግሪክ ፈላስፎች አፍቃሬ ጥበብ ነበሩ።

1፥23 የተሰቀለውን ክርስቶስን፤ 2፥2 ይመ። *ለአይሁድ መሰናክልም፤* አይሁድ ይጠብቁ የነበረው በመስቀል ተሰቅሎ የሚሞትን መሲሕ ሳይሆን፣ ድል አድራጊና ከምድራዊ አገዛዝ ነጻ አውጪ የሆነውን ነበር (ሐሥ 1፥6)። *ለአሕዛብ ደግሞ ሞኝነት፤* በግሪካውያንና በሮማውያን ዘንድ የተከበረ ሰው በመስቀል ላይ አይሰቀልም፤ በመሆኑም በስቅለት የተገደለ ወንጀለኛ፣ አዳኝ ይሆናል ማለት በእነርሱ ዘንድ ከቶ የሚታሰብ አይደለም።

1፥24 *ኀይል፤* ሮሜ 1፥4፡16፤ ማር 12፥24 ይመ። *ጥበብ፤* ቍ 30 ይመ። የተሰቀለው ክርስቶስ እንዲሁ ለሚያዩት ሞኝነት ቢመስልም፣ ማዳን የሚችል ኀይልና መለወጥ የሚችል ጥበብ ነው።

*1፥26-31፤* ድነት በሰው ጥረት እንደማይገኝ የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች ራሳቸው ሕያው ምስክር ናቸው፤ እንግዲህ አንድ ሰው ድነትን ካገኘ መመካት ያለበት በጌታ ነው (ቍ 31)።

1፥30 *በክርስቶስ ኢየሱስ … ከእርሱ የተነሣ ነው፤* ከክርስቶስ ጋር ኅብረትና አንድነት እንዲኖራችሁ የጠራችሁ እግዚአብሔር ነው። *ጽድቃችን፤* ጽድቅን ያገኘነው (በእግዚአብሔር ዘንድ እንደ ጻድቃን የተቈጠርነው) በኢየሱስ ክርስቶስ ባለን እምነት ነው (ሮሜ 5፥19 ይመ)። *ቅድስናችን፤* የቍ 2 ማብ ይመ። *ቤዛችንም፤* የሮሜ 3፥24 ማብ ይመ።

2፥1 *ወደ እናንተ በመጣሁ ጊዜ፤* ጳውሎስ በ51 ዓ.ም ገደማ ለመጀመሪያ ጊዜ ወደ ቆሮንቶስ የሄደበትን ወቅት ማለቱ ነው (ሐሥ 18)። ለረቀቀ ጥበብ ከልክ ያለፈ ቦታ ይሰጡ ስለነበር፣ ምናልባት የአጵሎስ ንግግር ልባቸውን ሳይማርከው አልቀረም (ሐሥ 18፥24-28)፤ *የእግዚአብሔርን ምስጢር፤* አንዳንድ የጥንት ቅጆች፣ "የእግዚአብሔር ምስክርነት" ይላሉ (ከቍ 7 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥2 *ኢየሱስ ክርስቶስን … ብቻ እንጂ ሌላ እንዳላውቅ፤* ጳውሎስ ከእነርሱ ጋር በነበረበት ጊዜ ትምህርቱም ሆነ ስብከቱ ክርስቶስ ብቻ እንዲሆን ወስኖ ነበር። *ኢየሱስ ክርስቶስን፤* 1፥30 ይመ። *የተሰቀለውን፣ እርሱን፤* 1፥17-18፡23 ይመ።

2፥4 *በመግለጥ፤* የግሪኩ ቃል የሚያመለክተው በፍርድ ቤት ክርክር ላይ ማስረጃ ማቅረብን ነው። የጳውሎስ ስብከት ተለይቶ የሚታወቀው ሰዎችን መለወጥ የሚችል የመንፈስ ቅዱስ ኀይል ከትምህርቱ ጋር መሆኑ ነው። *በሚያባብል የጥበብ ቃል አልነበረም፤* ይህ አባባል ሰባኪዎች፣ ያለጥናትና ያለ ዝግጅት እንዲያስተምሩ የሚያደፋፍር አይደለም፤ ጳውሎስ የተማረ ሰው መሆኑን ከመልእክቶቹ መገንዘብ የሚቻል ሲሆን፣ በአርዮስ ፋጎስ ሸንጎ ፊት ያደረገውም ንግግር (ሐሥ 17፥22-31 እና ማብ ይመ) ጥሩ ተናጋሪ እንደነበር ያስረዳል። ጳውሎስ እዚህ ላይ ለማለት የፈለገው፣ መንፈስ ቅዱስ የሰሚዎችን ልብ ካልከፈተ በቀር፣ ማራኪ አንደበት ብቻውን ፍሬ አልባ መሆኑን ነው። ሐዋርያው እንደ ግሪኮቹ አንደበተ ርቱዕ ተናጋሪዎች ወንጌልን በሚያበሥርበት ጊዜ ሁሉ፣ በራሱ ዕውቀትና በንግግር ችሎታው ላይ የተመሠረተ አልነበረም (የ1፥17 ማብ ይመ)።

## ከመንፈስ የተገኘ ጥበብ

[6]በበሰሉ ሰዎች መካከል ግን ጥበብን እን ናገራለን፤ ይሁን እንጂ የዚችን ዓለም ጥበብ ወይም የሚጠፉትን የዚችን ዓለም ገዦች ጥበብ አይደለም። [7]ነገር ግን ተሰውሮ የነበ ረውን የእግዚአብሔርን ምስጢር ጥበብ ነው፤ ይህም ጥበብ እግዚአብሔር ከዘመናት በፊት ለክብራችን አስቀድሞ የወሰነው ነው። [8]ከዚህ ዓለም ገዦች አንዳቸውም ይህን ጥበብ አል ተረዱትም፤ ቢረዱትማ ኖሮ የክብርን ጌታ ባልሰቀሉት ነበር። [9]ይሁን እንጂ፣ እንደ ተጻፈው፣

"ዐይን ያላየውን፣
ጆሮ ያልሰማውን፣
የሰውም ልብ ያላሰበውን፣
እግዚአብሔር ለሚወዱት አዘጋጅቶአል"

[10]እግዚአብሔር ግን ይህን በመንፈሱ አማካይ ነት ለእኛ ገልጦልናል።

*መንፈስም* የእግዚአብሔርን ጥልቅ ነገር እንኳ ሳይቀር ሁሉን ይመረምራል። [11]በው ስጡ ካለው ከራሱ መንፈስ በስተቀር ከሰው መካከል የአንድን ሰው ሐሳብ የሚያውቅ ማን አለ? እንደዚሁም ከእግዚአብሔር *መንፈስ* በስተቀር፣ የእግዚአብሔርን ሐሳብ የሚያውቅ ማንም የለም። [12]ከእግዚአብሔር የሆነውን *መን ፈስ* እንጂ፣ *የዓለምን መንፈስ* አልተቀበልን ምና፤ ይህም እግዚአብሔር በነጻ የሰጠንን እናውቅ ዘንድ ነው። [13]እኛ የምንናገረው ይህን ነው፤ ከሰው ጥበብ በተማርነው ቃል ሳይሆን፣ ከመንፈስ በተማርነው ቃል እንናገራለን፤ *መንፈሳዊ እውነትንም የምንገልጸው በመንፈሳዊ ቃል ነው*[a]። [14]*መንፈሳዊ ያልሆነ ሰው* ከእግዚአብሔር *መንፈስ* የሆነውን ነገር ሊቀበል አይችልም፤ ምክንያቱም እንዲህ ያለው ነገር ለእርሱ ሞኝነት ነው፤ በመንፈስም የሚመረመር ስለ ሆነ፣ ሊረዳው አይችልም። [15]*መንፈሳዊ ሰው* ግን ሁሉንም ነገር ይመረምራል፤ *ራሱ ግን በማንም አይመረመርም።*

[16]"*ያስተምረው ዘንድ*፣
የጌታን ልብ ማን ዐወቀው?"
እኛ ግን የክርስቶስ ልብ አለን።

2፥6 ቍ8፤ መዝ146፥4፤1ቆሮ1፥20፤ኤፌ4፥13፤ፊል3፥15፤ቈላ4፥12፤ዕብ5፥14፤6፥1፤ያዕ1፥4
2፥7 ቍ1፤ ሮሜ16፥25
2፥8 ቍ6፤ መዝ24፥7፤ሐሥ7፥2፤1ቆሮ1፥20፤ያዕ2፥1
2፥9 ኢሳ64፥4፤ 65፥17
2፥10 ማቴ13፥11፤ ዮሐ14፥26፤ 2ቆሮ12፥1:7፤ገላ1፥12፤ 2፥2፤ኤፌ3፥3:5
2፥11 ምሳ20፥27፤ ኤር17፥9
2፥12 ሮሜ8፥15፤ 1ቆሮ1፥20:27፤ ያዕ2፥5
2፥13 ቍ1:4፤ 1ቆሮ1፥17
2፥14 ዮሐ14፥17፤ 1ቆሮ1፥18
2፥15 1ቆሮ3፥1፤ ገላ6፥1
2፥16 ኢሳ40፥13፤ ዮሐ15፥15፤ ሮሜ11፥34
3፥1 ሮሜ7፥14፤ 1ቆሮ2፥14:15፤ 14፥20
3፥2 ዮሐ16፥12፤ ዕብ5፥12-14፤ 1ጴጥ2፥2
3፥3 ሮሜ13፥13፤ 1ቆሮ1፥11፤ገላ5፥20
3፥4 1ቆሮ1፥12
3፥5 ሐሥ18፥24፤ 1ቆሮ4፥1፤2ቆሮ6፥4፤ ኤፌ3፥7፤ቈላ1፥23:25

## በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የተከሠተ መለያየት

**3** ወንድሞች ሆይ፤ በክርስቶስ ገና *ሕፃናት* እንደ መሆናችሁ፣ እንደ *ሥጋውያን* እንጂ እንደ *መንፈሳውያን* ልናገራችሁ አልቻልሁም። [2]ገና ስላልጠነከራችሁ ወተት እንጂ ጠንካራ ምግብ አልመገብኋችሁም፤ አሁንም ቢሆን ገና ናችሁ። [3]አሁንም *ሥጋውያን* ናችሁ፤ በመካከላችሁ ቅናትና ክርክር አለ፤ ታዲያ፣ *ሥጋውያን* መሆናችሁ አይደለምን? ተግባ ራችሁስ *እንደ ማንኛውም ሰው* ተግባር መሆኑ አይደለምን? [4]ምክንያቱም አንዱ፣ "እኔ የጳውሎስ ነኝ"፣ ሌላው ደግሞ፣ "እኔ የአጵሎስ ነኝ" ቢል፣ ሰብአዊ ፍጡር ብቻ መሆናችሁ አይደለምን?

[5]ለመሆኑ አጵሎስ ምንድን ነው? ጳውሎስስ ምንድን ነው? ጌታ ለእያንዳንዳቸው በሰጣቸው መጠን የሚሠሩ አገልጋዮች ናቸው፤ እናንተም ወደ እምነት የመጣችሁት በእነርሱ አማካ

*[a]13 ወይም መንፈሳዊ እውነትንም ለመንፈሳዊ ሰው እንገልጻለን*

2፥6 *በበሰሉ፤* ያደጉና ጥበበኞች የሆኑ ክርስቲያኖችን ነው፤ በ 3፥1 ላይ፣ "ሕፃናት" ከተባሉት ጋር ያነጻጽሩ (ዕብ 5፥13-6፥3 ይመ)።

2፥7 *ምስጢር፤* ከሮሜ 16፥25-26፤ ኤፌ 3፥4-5፤ 1ጢሞ 3፥16 ጋር ያነጻጽሩ። ይህ ምስጢር ወይም ስውር ነገር በአንድ ወቅት ድብቅ ነበር፤ አሁን ግን እግዚአብሔር ለሕዝቡ ግልጥ ስላደረገው ገሃድ ወጥቶአል (ቍ 10)። ለማያምኑት ግን አሁንም ስውር ነው። *ለክብራችን፤* የእግዚአብሔር ጥበብ፣ እያንዳንዱን ክርስቲያን በመጨረሻ የክርስቶስ ክብር ተካፋይ እንዲሆን ያደርገዋል (ሮም 8፥17)።

2፥8 *ከዚህ ዓለም ገዦች፤* እንደ ካህናት አለቆች (ሉቃ 24፥20)፣ እንደ ጲላጦስና እንደ ሄሮድስ አንቲጳስ ያሉት ናቸው (ከሐሥ 4፥27 ጋር ያወዳድሩ)። *የክብርን ጌታ ባልሰቀሉት፤* እዚህ ላይ መስቀልና በመስቀል ላይ የተሰቀለው ጌታ ክብር ተነጻጽረዋል።

2፥9 *እግዚአብሔር ... አዘጋጅቶአል፤* ይህ ሐረግ የሚናገረው አሁንና ወደፊት ስለምናገኘው በረከት ሳይሆን አይቀርም (ከቍ 7:12 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥10 *መንፈስ ... ሁሉን ይመረምራል፤* የሚመረምረው የማያውቀው ነገር ኖሮ፣ ያን ለማወቅ አይደለም፤ እርሱ ሁሉን ያውቃልና። ይልቁንም እርሱ የእግዚአብሔር ባሕርይና የጸጋው ዕቅድ ገንዘቡ ስለ ሆነ፣ እዚህ ላይ የተነገረውን መግለጥ ይፋ ለማድረግ ይቻለዋል።

2፥12 *የዓለምን መንፈስ፤* ከቍ 6 ("የዚህችን ዓለም ጥበብ") ጋር ያወዳድሩ፤ ከእግዚአብሔር ጨርሶ የተለየውን የሰውን ጥበብ መንፈስ ወይም ወደ ኀጢአት የሚያዘነብለውን የሰውን ክፉ ባሕርይ ማለት ነው (ሮሜ 8፥6-7)።

2፥13 *ከመንፈስ በተማርነው ቃል፤* ጳውሎስ ያበሠረውን ወንጌል የተናገረው መንፈስ ቅዱስ በሰጠው ቃል ነው፤ በመሆኑም መንፈሳዊ እውነት ከመንፈሳዊ ቃል ጋር በሚገባ ተገናዝቦ እናገኛለን።

*2፥14-3፥4፤* ይህ ክፍል ብዙዎች ለምን እውነተኛውን ጥበብ መረዳት እንዳልቻሉ ይገልጻል (2፥9)፤ ምክንያቱም እንዲህ ያለውን ጥበብ ማስተዋል የሚችሉት መንፈሳውያን ወይም የበሰሉ ክርስቲያኖች ብቻ ናቸው (2፥14-16 ይመ፤ ከቍ 6 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይሁን እንጂ የቆሮንቶስ ምእመናን ሥጋውያን ወይም ያልበሰሉ አማኞች ነበሩ (3፥1-4)፤ በወንጌል ሰባክያን ስም ቡድን ለይተው መከፋፈላቸው በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ገና ያልበሰሉ መሆናቸውን ያሳያል (3፥3-4)።

2፥14 *መንፈሳዊ ያልሆነ ሰው፤* በይሁዳ መልእክት ቍ 19 ላይ፣ "የሥጋ ምኞትን የሚከተሉ" እንደተባሉት ዐይነት ማለት ነው (ከሮሜ 8፥9 ጋር ያወዳድሩ)። ክርስቲያን ያልሆነ ሰው ሕይ ወቱ በሥጋዊ፣ በዓለማዊና በተፈጥሮአዊ ነገር የተወረሰ ነው። የመንፈስ ቅዱስ ማደሪያ ባለመሆኑ፣ ከመንፈስ የሆነውን እውነት በደስታ ሊቀበል አይችልም። እንዲህ ያለ ሰው፣ ዳግመኛ መወለድ ያስፈልገዋል (ዮሐ 3፥1-8፤ ቲቶ 3፥5-6)። *ሞኝነት፤* 1፥18 ይመ።

2፥15 *መንፈሳዊ ሰው፤* የበሰለ ክርስቲያን ማለት ነው (ቍ 16)። *ራሱ ግን በማንም አይመረመርም፤* መንፈስ ቅዱስ ያላደረበት ሰው፣ የመንፈሳዊውን ሰው ሐሳብ ለማወቅ ብቃት የለውም፤ በመሆኑም አማኞች በማያምኑ ሰዎች መመርመር አይችሉም።

3፥1 *ወንድሞች፤* የ1፥10 ማብ ይመ። *ሥጋውያን፤* የ2፥14-3፥4 ማብ ይመ። *መንፈሳውያን፤* የ2፥15 ማብ ይመ።

3፥2 *ወተት እንጂ ጠንካራ ምግብ አልመገብኋችሁም፤* የዕብ 5፥12-14 ማብ ይመ።

3፥3 *እንደ ማንኛውም ሰው፤* እንደ እግዚአብሔር ሰው ሳይሆን እንደዚህ ዓለም ሰው ይመላለሱ ነበር፤ ይመሩ የነበረውም በዓለማዊ ሥርዐትና መስፈርት ነበር።

3፥4 *እኔ የጳውሎስ ነኝ ... እኔ የአጵሎስ ነኝ፤* 1፥12 ይመ።

ይነት ነው:: [6]እኔ ተከልሁ፤ አጵሎስ ውሃ አጠጣ፤ ያሳደገው ግን እግዚአብሔር ነው:: [7]ስለዚህ የሚያሳድግ እግዚአብሔር እንጂ፣ የሚተክልም ሆነ ውሃ የሚያጠጣ ምንም አይደለም:: [8]የሚተክልም ሆነ የሚያጠጣ አንድ ናቸው፤ እያንዳንዱም እንደ ሥራው መጠን የራሱን ሽልማት ይቀበላል:: [9]እኛ ከእግዚአብሔር ጋር አብረን የምንሠራ ነንና፤ እናንተም የእግዚአብሔር ዕርሻ ናችሁ፤ የእግዚአብሔር ሕንጻ ናችሁ::

[10]ከእግዚአብሔር በተሰጠኝ ጸጋ መጠን፣ እንደ አንድ ብልኅ ግንበኛ መሠረትን ጣልሁ፤ ሌላውም በላዩ ላይ ይገነባል፤ ነገር ግን እያንዳንዱ እንዴት እንደሚገነባ መጠንቀቅ አለበት:: [11]ምክንያቱም አንድ ጊዜ ከተመሠረተው መሠረት በቀር ሌላ መሠረት መጣል የሚችል ማንም የለም፤ ይህም መሠረት ኢየሱስ ክርስቶስ ነው:: [12]ማንም በዚህ መሠረት ላይ በወርቅ ወይም በብር፣ በከበረ ድንጋይ ወይም በዕንጨት፣ በሣር ወይም በአገዳ ቢያንጽ፣ [13]ሥራው እንዴት እንደ ሆነ ይታያል፤ ምክንያቱም ያ ቀን ወደ ብርሃን ያመጣዋል:: በእሳት ስለሚገለጥ እሳቱ የእያንዳንዱን ሰው ሥራ ምንነት ይፈትናል:: [14]ማንም የገነባው ሥራ ቢጸናለት ሽልማቱን ይቀበላል፤ [15]ሥራው የተቃጠለበት ግን ሽልማት ይቀርበታል፤ እርሱ ራሱ ግን ይድናል፤ ይሁን እንጂ የሚድነው በእሳት ውስጥ በጭንቅ እንደሚያልፍ ሆኖ ነው::

[16]እናንተ ራሳችሁ የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ እንደ ሆናችሁ፣ የእግዚአብሔርም[m] መንፈስ በውስጣችሁ እንደሚኖር አታውቁምን? [17]ማንም የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስ ቢያፈርስ እግዚአብሔር እርሱን ያፈርሰዋል፤ የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ቅዱስ ነውና፤ ያም ቤተ መቅደስ እናንተ ናችሁ::

[18]ማንም ራሱን አያታልል፤ ከእናንተ ማንም በዚህ ዓለም ጥበበኛ የሆነ ቢመስለው፣ ጥበበኛ ይሆን ዘንድ ራሱን እንደ ሞኝ ይቍጠር:: [19]የዚህ ዓለም ጥበብ በእግዚአብሔር ፊት ሞኝነት ነውና፤ እንዲህ ተብሎ ተጽፎአልና፤ "እርሱ ጥበበኞችን በራሳቸው ተንኰል ይይዛቸዋል፤" [20]በሌላ ስፍራ ደግሞ፣ "ጌታ የጥበበኞች ሐሳብ ከንቱ መሆኑን ያውቃል" ተብሎ ተጽፎአል፤ [21]እንግዲህ ማንም በሰው አይመካ:: ሁሉ ነገር የእናንተ ነውና፤ [22]ጳውሎስም ሆነ አጵሎስ ወይም ኬፋ[n]፣ ዓለምም ሆነ ሕይወት ወይም ሞት፣ አሁን ያለውም ሆነ ወደ ፊት የሚመጣው፣ ሁሉ የእናንተ ነው፤ [23]እናንተም የክርስቶስ ናችሁ፤ ክርስቶስም የእግዚአብሔር ነው::

## የክርስቶስ ሐዋርያት

**4** እንግዲህ ሰው ሁሉ እኛን እንደ ክርስቶስ አገልጋዮችና እንደ እግዚአብሔር ምስጢር ባለ ዐደራዎች ሊቈጥረን ይገባል:: [2]ባለ ዐደራዎችም ታማኝ ሆነው መገኘት አለባቸው:: [3]በእናንተም ሆነ በሰዎች የፍርድ ሸንጎ ቢፈረድብኝ እኔ በበኩሌ ግድ የለኝም፤ እኔ እንኳ በራሴ ላይ አልፈርድም:: [4]ኅሊናዬ ንጹሕ ነው፤ ይህ ግን ጥፋት አልባ መሆኔን አያረ

3፥6 ሐሥ18፥4-11፤ 1ቆሮ4፥15፤9፥1፤15፥1
3፥8 ቍ14፤ መዝ18፥20፤62፥12፤ ማቴ25፥21፤ 1ቆሮ9፥17
3፥9 ኢሳ61፥3፤ ማር16፥20፤ 2ቆሮ6፥1፤ኤፌ2፥20-22፤1ተሰ3፥2፤ 1ጴጥ2፥5
3፥10 ሮሜ12፥3፤ 15፥20፤ኤፌ2፥20
3፥11 ኢሳ28፥16፤ ኤፌ2፥20
3፥13 ዘኍ31፥22፡23፤ኤር23፥28፥29፤ ሚል3፥3፤1ቆሮ1፥8፤ 4፥5፤2ተሰ1፥7-10፤ 2ጢሞ1፥12፡18፤4፥8
3፥14 ቍ8
3፥15 ይሁ23
3፥16 ሮሜ8፥9፤ 1ቆሮ6፥19፤ዒሠ 2ቆሮ6፥16፤ኤፌ2፥21፡ 22፤ዕብ3፥6
3፥18 ኢሳ5፥21፤ 1ቆሮ1፥20፤8፥2፤ ገላ6፥3
3፥19 ቍ18፤ ኢዮ5፥13፤ ሮሜ1፥ 22፤ 1ቆሮ1፥20፡27
3፥20 መዝ94፥11
3፥21 ሮሜ8፥32፤ 1ቆሮ4፥6
3፥22 ቍ5፡6፤ ሮሜ8፥38፤1ቆሮ1፥12
3፥23 1ቆሮ15፥23፤ 2ቆሮ10፥17፤ገላ3፥29
4፥1 ሮሜ16፥25፤ 1ቆሮ3፥5፤9፥17፤ ቲቶ1፥7
4፥4 ሐሥ23፥1፤ሮሜ2፥13፤2ቆሮ10፥18

[n]22 ጴጥሮስ ማለት ነው

3፥6 *እኔ ተከልሁ፤* ሐሥ 18፥4-11 ይመ:: የጳውሎስ ተግባር ማንም ወንጌልን ባልሰበከበት ስፍራ መስበክ:: *አጵሎስ ውሃ አጠጣ፤* ሐሥ 18፥24-28 ይመ:: የአጵሎስ ተልእኮ በተመሠረቱ አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ ጳውሎስ ወደ ጌታ የመጠለሳቸውን ምዕመናን ማነጽ ነበር::

3፥9 *የእግዚአብሔር ዕርሻ፤* ክርስቲያኖች የእግዚአብሔር ዕርሻ ተብለው ተጠርተዋል:: *የእግዚአብሔር ሕንጻ፤* በሌላም በኩል የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ተብለዋል (ቍ 16-17):: ጳውሎስና አጵሎስ የሚሠሩበት ዕርሻም ሆነ ሕንጻ ባለቤቱ እግዚአብሔር ነው::

3፥10 *መሠረትን ጣልሁ፤* የተሰቀለውን ክርስቶስን በመስበክ ነው (2፥2):: *ሌላውም፤* አጵሎስን ነው::

3፥12 *በወርቅ ወይም በብር፣ በከበረ ድንጋይ፤* በእግዚአብሔር ፍርድ ፊት መቆም የሚችለውን ክቡርና ዘላቂ ሥራ የሚያመለክት ሲሆን፣ የጤናማ ክርስቲያናዊ አስተምህሮና ኑሮ ምሳሌ ናቸው:: *በዕንጨት፣ በሣር ወይም በአገዳ፤* በእግዚአብሔር ፍርድ ፊት መቆም የማይችለውን ከንቱ ሥራ የሚያሳይ ሲሆን፣ የደካማና ሕይወት የለሽ አስተምህሮና ኑሮ ምሳሌ ናቸው::

3፥13፤ ከ4፥5፤ 2ቆሮ 5፥10 ጋር ያነጻጽሩ:: *ያ ቀን፤* የ1፥8 ማብ ይመ:: *እሳት፤* የእግዚአብሔር ፍርድ ነው፤ የአንዳንድ አማኞች ሥራ በፍርድ ፊት መቆም ሲችል፣ የሌሎች ግን ይጠፋል፤ ይህም ትክክለኛውን የእግዚአብሔርን ቃል ማስተማር ምን ያህል አስፈላጊ እንደ ሆነ ያሳያል::

3፥15 *ይቀርበታል፤* የድካሙን ዋጋ ያጣል ማለት ነው (ቍ 14):: *በእሳት ውስጥ በጭንቅ እንደሚያልፍ፤* ምናልባት የግሪኮች አነጋገር ዘዬ ሊሆን ይችላል፤ ትርጕሙም፣ "በስንት ጣርና ምጥ" ማለት ሲሆን፣ አንድ ሰው ሥራው በእግዚአብሔር ፍጹም የፍትሕና ፍርድ እሳት ሲቃጠልበት እርሱ ግን በጭንቅ መዳኑን ያሳያል::

3፥16 *የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፤* የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን ነው፤ እዚህ ላይ ጳውሎስ ለመግለጽ የፈለገው እያንዳንዱ የመልእክቱ ተደራሲ የመንፈስ ቅዱስ ማደሪያ መሆኑን ሳይሆን፣ በጥቅሉ ስለ ጉባኤው ነው::

3፥17 *እግዚአብሔር እርሱን ያፈርሰዋል፤* እንዲህ ያለው ከንቱና ፍሬ ቢስ ሠራተኛ፣ ከእውነተኞቹ የጌታ አገልጋዮች መካከል እንዳልሆነ የሚመለክት ከባድ አነጋገር ነው:: ይህም በቍ 15 ላይ፣ ሥራው ከንቱ ከሆነበት፣ እርሱ ራሱ ግን ከሚድነው ክርስቲያን ጋር የሚነጻጸር ሐሳብ ነው:: ከም1-4 ባለው ክፍል ጳውሎስ የሚናገረው ቤተ ክርስቲያንን በቅናትና በክርክር ስለሚከፋፈሉ ሰዎች እንደመሆኑ (1፥11-12)፣ እዚህም ላይ የሚያወሳው ስለ እነርሱ ነው::

3፥18 *ጥበበኛ ይሆን ዘንድ፤* ከ1፥21፡24 ጋር ያነጻጽሩ:: *ራሱን እንደ ሞኝ ይቍጠር፤* ከሰዎች ጥበብና ከዚህ ዓለም መርህ ርቆ፣ በእግዚአብሔር ጥበብ መመራት ማለት ነው፤ ከ1፥18 ጋር ያነጻጽሩ::

3፥21 *በሰው፤* የአንድ ሰው ደቀ መዝሙር በመሆን ማለት ነው (1፥12፤ 3፥4 ይመ፤ ከ1፥31፤ ከ4፥6 ጋር ያነጻጽሩ):: *ሁሉ የእናንተ ነውና፤* እነዚህ ሁሉ ክርስቲያን መሪዎች የመላ ቤተ ክርስቲያኒቱ አገልጋዮች ናቸው፤ የትኛውም ቡድን አንድን የቤተ ክርስቲያን መሪ የራሱ ብቻ አድርጎ መቍጠር አይገባውም (ቍ 22-23 ይመ)::

3፥23 *እናንተም የክርስቶስ ናችሁ፤* ከክርስቶስ ጋር ኅብረት አግኝታችኋል፤ የክርስቶስም ሆናችኋል ማለት ነው:: *ክርስቶስም የእግዚአብሔር ነው፤* ክርስቶስ ከእግዚአብሔር አብና (ዮሐ 10፥30) ከእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ (2ቆሮ 13፥14) ጋር አንድነት አለው:: እንዲሁም ክርስቲያኖች ከእውነተኛ የቤተ ክርስቲያን መሪዎችና (ቍ 22) ከተቀሩት የሥላሴ አካላት ጋር አንድነት ካላቸው ከክርስቶስ (ቍ 23) ጋር ኅብረት አላቸው::

4፥1 *ምስጢር፤* ሰው በራሱ ጥበብ ሊደርስበት የማይችል ነገር ግን እግዚአብሔር ለሕዝቡ የገለጠው ነው (የሮሜ 11፥25 ማብ ይመ):: *ባለ ዐደራዎች፤* የግሪኩ ቃል፣ "የቤት አስተዳዳሪ" ወይም፣ "መጋቢ" የሚል ትርጕም አለው::

4፥3 *እኔ እንኳ በራሴ ላይ አልፈርድም፤* ፍርዱ የሰው

ጋግጥም፤ በእኔ ላይ የሚፈርድ ጌታ ነው:: [5]ስለዚህ ጊዜው ሳይደርስ በምንም ነገር አትፍረዱ፤ ጌታ እስኪመጣ ጠብቁ:: እርሱ በጨለማ ውስጥ የተሰወረውን ወደ ብርሃን ያመጣዋል፤ በሰዎች ልብ ውስጥ ያለውንም ሐሳብ ይገልጠዋል:: በዚያን ጊዜ እያንዳንዱ ሰው የሚገባውን ምስጋና ከእግዚአብሔር ዘንድ ይቀበላል::

[6]እንግዲህ ወንድሞች ሆይ፤ ለእናንተ ጥቅም ብዬ በዚህ ጉዳይ እኔን ራሴንና አጵሎስን ምሳሌ አድርጌ አቅርቤላችኋለሁ፤ ይህንም ያደረግሁት፣ "ከተጻፈው አትለፍ" የሚለውን ከእኛ እንድትማሩ ነው:: ስለዚህ አንዱን ሰው ከሌላው አብልጣችሁ አትመኩበት:: [7]ለመሆኑ፣ አንተን ከሌላው እንድትበልጥ ያደረገህ ማን ነው? ያልተቀበልኸው የራስህ የሆነ ነገር ምን አለ? ከተቀበልህ ታዲያ፣ እንዳልተቀበልህ ለምን ትመካለህ?

[8]አሁንስ የሚያስፈልጋችሁን ሁሉ አግኝታችኋል! ሀብታምም ሆናችኋል! ከእኛም ተለይታችሁ ነግሣችኋል! በእርግጥ ብትነግሡማ እኛም ከእናንተ ጋር በነገሥን ነበር፤ [9]ምክንያቱም እግዚአብሔር እኛን ሐዋርያቱን፣ ሞት እንደ ተፈረደባቸው ሰዎች ከሰው ሁሉ መጨረሻ ያሰለፈን ይመስለኛል፤ ለዓለም ሁሉ መላእክትም ለሰዎችም ትርኢት ሆነናል:: [10]እኛ ስለ ክርስቶስ ብለን ሞኞች ነን፤ እናንተ ግን በክርስቶስ ጥበበኞች ናችሁ፤ እኛ ደካሞች ነን፤ እናንተ ግን ብርቱዎች ናችሁ፤ እናንተ የተከበራችሁ ናችሁ፤ እኛ ግን የተዋረድን ነን:: [11]እስከዚህ ሰዓት ድረስ እንራባለን፤ እንጠማለን፤ እንራቈታለን፤ እንደበደባለን፤ ያለመጠለያ እንንከራተታለን፤ [12]በገዛ እጃችን እየሠራን እንደክማለን:: ሲረግሙን እንመርቃለን፤ ሲያሳድዱን እንታገሣለን፤ [13]ስማችንን ሲያጠፉ መልካም እንመልሳለን:: እስከ አሁን ድረስ የዓለም ጉድፍ፣ የምድር ጥራጊ ሆነናል::

[14]ይህን የምጽፍላችሁ እንደ ተወደዳችሁ ልጆቼ አድርጌ ልመክራችሁ እንጂ ሳሳፍራችሁ ብዬ አይደለም:: [15]ምንም እንኳ በዐሥር ሺህ የሚቈጠሩ ሞግዚቶች በክርስቶስ ቢኖሯችሁም፣ ብዙ አባቶች ግን የሏችሁም፤ በወንጌል አማካይነት በክርስቶስ ኢየሱስ ወልጄአችኋለሁና:: [16]ስለዚህ እኔን እንድትመስሉ እለምናችኋለሁ:: [17]እንግዲህ በጌታ የተወደደውንና የታመነውን ልጄን ጢሞቴዎስን የላክሁላችሁ በዚህ ምክንያት ነው፤ እርሱም በየስፍራው በሚገኙ አብያተ ክርስቲያናት ሁሉ ከማስተምረው ትምህርት ጋር የሚስማማውን፣ በክርስቶስ ኢየሱስ ያለውን የሕይወት አካሄዴን ያሳስባችኋል::

[18]ከእናንተ አንዳንዶቹ ወደ እናንተ የማልመጣ መስሎአቸው ታብየዋል፤ [19]ይሁን እንጂ የጌታ ፈቃድ ቢሆን ፈጥኜ ወደ እናንተ እመጣለሁ፤ ከዚያም እነዚህ ትዕቢተኞች የሚናገሩትን ብቻ ሳይሆን፣ ምን ኀይል እንዳላቸውም ማየት እሻለሁ:: [20]ምክንያቱም የእግዚአብሔር መንግሥት የወሬ ጉዳይ ሳይሆን የኀይል ጉዳይ ነው:: [21]ለመሆኑ የምትፈልጉት የቱን ነው? በትር ይዤ ልምጣ? ወይስ በፍቅርና በገርነት መንፈስ?

### አሳፋሪ ኀጢአት በቤተ ክርስቲያን

**5** በመካከላችሁ የዝሙት ርኵሰት እንዳለ በእርግጥ ይወራል፤ እንዲህ ያለው ርኵሰት በአረማውያን ዘንድ እንኳ የማይታይ ነው፤ የአባቱን ሚስት ያገባ ሰው አለና::

4፥5 ኢዮ12፥22፤ መዝ90፥8፤ ማቴ7፥1:2፤ ሮሜ2፥29፤ 1ቆሮ3፥13፤ 1ተሰ2፥19
4፥6 1ቆሮ1፥12: 19:31፤3፥4:19:20
4፥7 ዮሐ3፥27፤ ሮሜ12፥3:6
4፥8 ራእ3፥17:18
4፥9 መዝ71፥7፤ ሮሜ8፥36፤ዕብ10፥33
4፥10 ሐሥ17፥18፤ 26፥24፤1ቆሮ1፥18፤ 2፥3፤3፥18፤ 2ቆሮ11፥19
4፥11 ሮሜ8፥35፤ 2ቆሮ11፥23-27
4፥12 ማቴ5፥44፤ ሐሥ18፥3፤ ሮሜ12፥14፤1ጴጥ3፥9
4፥13 ኢር20፥18፤ ሰቆ3፥45
4፥14 1ቆሮ6፥5፤ 15፥34፤1ተሰ2፥11፤2 ተሰ3፥14
4፥15 ቍ14፤ 1ቆሮ9፥12:14:18:2 3፤15፥1
4፥16 1ቆሮ11፥1፤ ፊል3፥17፤4፥9፤ 1ተሰ1፥6፤2ተሰ3፥7:9
4፥17 ሐሥ16፥10፤ 1ቆሮ7፥17፤16፥10፤1 ጢሞ1፥2
4፥18 ቍ21፤ኢር43፥2
4፥19 ሐሥ18፥21፤ 1ቆሮ16፥5:6፤ 2ቆሮ1፥15:16
4፥20 ሮሜ14፥17፤ 15፥13
4፥21 2ቆሮ1፥23፤ 2፥1፤13፥2:10
5፥1 ዘሌ18፥8፤ ዘዳ22፥30፤27፥20

ፍርድ ብቻ ይሆናል፤ ኅሊናውም ሊሳሳት ይችላል (ቍ 4)፤ ትክክለኛ ፍርድ መስጠት የሚችል ግን እግዚአብሔር ብቻ ነው::

4፥5 *ጊዜው፤* እግዚአብሔር በአማኞች ላይ የሚፈርድበት ጊዜ ነው (3፥13 ይመ):: *ሐሳብ ይገልጠዋል፤* ከመዝ 19፥12፤ 139፥23-24፤ ዕብ 4፥12-13 ጋር ያነጻጽሩ::

4፥6 *በዚህ ጉዳይ፤* 3፥5-4፥5 ይመ:: *ከተጻፈው፤* በቅዱሳት መጻሕፍት ከተደነገገው ማለት ነው:: ስለ ሰው ያለን አመለካከት በመጽሐፍ ቅዱሳዊ መሆን አለበት (ከቍ 7፤ 1፥9:31፤ 3፥19-20፤ ሮሜ 12፥3 ጋር ያነጻጽሩ)፤ የሰውን ደካማነትና ውሱንነት መገንዘብ ይኖርብናል:: *የሚለውን፤* በአይሁድ ረበናት (መምህራን) ዘንድ የተለመደ ብሂል ሳይሆን አይቀርም:: *አትመኩበት፤* ለመለያየት መንሥኤ ከሚሆኑት ምክንያቶች አንዱ ነው::

*4፥8፤* የቆሮንቶስ ሰዎች ከእብሪታቸውና በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ካለመብሰላቸው የተነሳ፣ ምን ያህል ምስኪን መሆናቸውን እንዲያስተውሉ፣ ጳውሎስ ምፀትና ሥላቅን ይጠቀማል፤ እዚህ ላይ ጳውሎስ ስለ ቆሮንቶስ ምእመናን የሚናገረው ከሐዋርያት ጋር በማነጻጸር ነው::

4፥9 *ሐዋርያቱን፤* የ1፥1 ማብ ይመ:: *ትርኢት፤* "ቲያትር" የሚለው የአማርኛ ቃል የተወረሰው እዚህ ላይ ከገባው የግሪክ ቃል ነው:: ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚያወሳው የጥንት ሮማውያን ሰውን ከሰው ወይም ሰውን ከእንስሳ እያታገሉ የሚያዩትን ትርኢት (ምናልባትም አንድ የሮም ጀኔራል ድል አድርጎ ወደ አገሩ ሲመለስ የሚደረግለትን ታላቅ አቀባበልና ሰልፍ) ሳይሆን አይቀርም:: ሐዋርያት ወደ ትርኢት ማሳያው ስፍራ ገብተው እስከ ሞት ድረስ ሲፋለሙ፣ መላው ዓለምና መላእክትም ይህንኑ ትርኢት ሲመለከቱ ሥዕላዊ በሆነ አነጋገር ይገልጻል::

*4፥10፤ ተጨማሪ ምፀታዊ አነጋገር ነው::*

*4፥11-13፤* ጳውሎስ ይህን ደብዳቤ እስከ ጻፈበት ጊዜ ድረስ፣ በኤፌሶን የደረሰበት መከራና ሥቃይ ምን ይመስል እንደ ነበር ቍልጭ አድርጎ ዝርዝር ሁኔታውን ይገልጻል::

4፥12 *በገዛ እጃችን እየሠራን እንደክማለን፤* ጳውሎስ ይተዳደር የነበረው ድንኳን በመስፋት ነበር (ሐሥ 18፥3 ይመ፤ ከ20፥34-35፤ 1ቆሮ 9፥6:18 ጋር ያነጻጽሩ):: *እንመርቃለን፤* ማቴ 5፥44 ይመ:: *እንታገሣለን፤* በበቀል ፈንታ ማለት ነው::

4፥14 *እንደ ተወደዳችሁ ልጆቼ፤* ቍ 15 ይመ::

4፥15 *ወልጄአችኋለሁና፤* 3፥6:10 ይመ::

4፥18 *ከእናንተ አንዳንዶቹ፤* አንዳንድ የቆሮንቶስ ሰዎች የጳውሎስን ሥልጣን በማጣጣልና (9፥1-3 ይመ) ወላዋይ ሰው እንደ ሆነ በማስተማር (2ቆሮ 1፥17) አገልግሎቱን ከንቱ ለማድረግ (2ቆሮ 10፥10) ይሞክሩ ነበረ::

4፥19 *ትዕቢተኞች፤* 5፥2 ይመ::

4፥20 *የእግዚአብሔር መንግሥት፤* እግዚአብሔር በአሁኑ ዘመን በሕዝቡ ሕይወት ውስጥ ያለውን አገዛዝና አመራር የሚያሳይ ሲሆን፣ በክርስቶስ ያገኘነውን አዲስ ሕይወትና (2ቆሮ 5፥17) የአዲስ ልደት ኀይል (ዮሐ 3፥3-8) ያመለክታል፤ ይህም ለክርስቶስና ለቤተ ክርስቲያኑም ሙሉ በሙሉ በተሰጠ የትሕትና ሕይወትን ይገለጣል:: *የወሬ ጉዳይ ሳይሆን የኀይል ጉዳይ ነው፤* ፍሬ ቢስ የሆነ ከንቱ ልፍለፋ ከእውነተኛው የመንፈስ ቅዱስ ኀይል ጋር ተነጻጽሮአል::

5፥1 *በአረማውያን ዘንድ እንኳ የማይታይ፤* ሮማዊው አንደበተ ርቱዕ ሲሴሮ፣ በሮማውያን ኅብረተ ሰብ ዘንድ የሥጋ ዝምድና ባላቸው ሰዎች መካከል የሩካቤ ሥጋ ተሰምቶ እንደማይታወቅ ይናገራል:: *የአባቱን ሚስት፤* እናቱን በማለት ፈንታ በዚህ መልክ መገለጹ፣ ሴትዮዋ የእንጀራ እናቱ መሆኗን ያመለክታል፤ ብሉይ ኪዳንም እንዲህ ያለውን ነገር ይከለክላል (ዘሌ 18፥8፤ ዘዳ 22፥30፤ 27፥20)::

[2]ደግሞም ታብያችኋል! ይልቅስ ሐዘን ተሰምቶአችሁ፣ ይህን ድርጊት የፈጸመውን ሰው ከመካከላችሁ ልታስወግዱት አይገባምን? [3]ምንም እንኳ እኔ በአካል አብሬያችሁ ባልሆንም፣ በመንፈስ ግን ከእናንተ ጋር ነኝ፤ ልክ አብሬያችሁ እንዳለሁ ሆኜ፣ ይህን ባደረገው ሰው ላይ አሁኑኑ ፈርጀበታለሁ። [4]በምትሰበሰቡበት ጊዜ እኔም በመንፈስ ከእናንተ ጋር ስለምሆን፣ በጌታችን በኢየሱስ ስምና በመካከላችሁ በሚገኘው በጌታችን በኢየሱስ ኀይል፣ [5]ሥጋው[a] ጠፍቶ መንፈሱ በጌታ ቀን ትድን ዘንድ፣ እንደዚህ ዐይነቱ ለሰይጣን ይሰጥ።

[6]መመኪያችሁ መልካም አይደለም። ጥቂት እርሾ ብዙውን ሊጥ እንደሚያቦካው አታውቁምን? [7]አሁን ያለ እርሾ እንደ ሆናችሁ ሁሉ አዲስ ሊጥ እንድትሆኑ አሮጌውን እርሾ አስወግዱ፤ የፋሲካ በጋችን የሆነው ክርስቶስ ተሠውቶአልና። [8]ስለዚህ በዓሉን ግፍና ክፋት በሞላበት እርሾ፣ በአሮጌ እርሾ ሳይሆን፣ እርሾ በሌለበት ቂጣ በቅንነትና በእውነት እናክብር።

[9]ከሴሰኞች ጋር እንዳትተባበሩ በመልእክቴ ጽፌላችሁ ነበር፤ [10]እንዲህም ስል በጠቅላላው ከዚህ ዓለም ሴሰኞች ወይም ስግብግቦችና ቀማኞች፣ ወይም ከጣዖት አምላኪዎች ጋር አትተባበሩ ለማለት አይደለም፤ እንደ ዚያማ ቢሆን ከዚህ ዓለም ጨርሶ መለየት ያስፈልጋችሁ ነበር። [11]ነገር ግን አሁን የጻፍሁላችሁ፣ "ወንድም ነኝ" እያለ ከሚሴስን ወይም ከሚስገበገብ ወይም ጣዖትን ከሚያመልክ ወይም ከሚሳደብ ወይም ከሚሰክር ወይም ከሚቀማ ጋር እንዳትተባበሩ ነው፤ ከእንደዚህ ዐይነቱ ሰው ጋር ምግብ እንኳ አትብሉ።

[12]ከቤተ ክርስቲያን ውጪ ባሉት ሰዎች ላይ ለመፍረድ እኔን ምን አገባኝ? በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ባሉት ሰዎች ላይ እናንተ አትፈርዱምን? [13]ከቤተ ክርስቲያን ውጪ ባሉት ላይ የሚፈርድ ግን እግዚአብሔር ነው፤ እንግዲህ፣ "ክፉውን ሰው ከመካከላችሁ አስወግዱት።"

## መካሰስ በክርስቲያኖች መካከል

**6** ከመካከላችሁ አንድ ሰው ከሌላው ጋር ሙግት ቢኖረው፣ ጉዳዩን በቅዱሳን ፊት

[a]5 ወይም ኀጢአተኛ ተፈጥሮው ወይም አካሉ

5፥2 ቆ 13፤ 2ቆሮ7፥7-11
5፥3 ቈላ2፥5፤ 1ተሰ2፥17
5፥4 2ተሰ3፥6
5፥5 ማቴ4፥10፤ ቆሮ1፥8፤1ጢሞ1፥20
5፥6 ማቴ16፥6: 12፤ገላ5፥9፤ያዕ4፥16
5፥7 ዘፀ12፥3-6: 21፤ማር14፥12፤ 1ጴጥ1፥19
5፥8 ዘፀ12፥14:15፤ ዘዳ16፥3
5፥9 ኤፌ5፥11፤ 2ተሰ3፥6:14
5፥10 1ቆሮ10፥27
5፥11 ሮሜ7፥1፤ 16፥17፤ 1ቆሮ10፥7:14
5፥12 ቍ3-5፤ ማር4፥11፤ 1ቆሮ6፥ 1-4
5፥13 ዘዳ13፥5፤ 17፥7፤19፥19፤ 22፥21:24፤24፥7፤ መሳ20፥13
6፥1 ማቴ18፥17

5፥2 *ታብያችኋል፤* የእግዚአብሔርን ጸጋ በትክክል ካለመረዳታቸው የተነሣ፣ ባገኙት ነጻነት ተኵራርተው እንደ ነበር ያሳያል። *ከመካከላችሁ ልታስወግዱት፤* ከቤተ ክርስቲያን ልትለዩት ማለት ነው (ከዮሐ 9፥22 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥4 *በምትሰበሰቡበት ጊዜ ... በጌታችን በኢየሱስ ስም፤* የቆሮንቶስ ሰዎች አሳፋሪ ተግባር በፈጸመ ሰው ላይ መፍረድ ያለባቸው፣ በጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሥልጣን ነው። *በመካከላችሁ በሚገኘው በጌታችን በኢየሱስ ኀይል፤* የኢየሱስ ክርስቶስ ኀይል በመካከላቸው የሚገኘው፣ በቃሉና በመንፈስ ቅዱስ አማካይነት ነው።

5፥5 *ሥጋው ጠፍቶ፤* ቤተ ክርስቲያን በተሰጣት ሥልጣን አሳፋሪ ተግባር የፈጸመውን ሰው ከማኅበረ ምእመና የምታስወግደው፣ በድርጊቱ በመጸጸት ንስሓ ገብቶ የቀድሞውን ክፉ መንገድ እንዲተው ነው። በሌላ በኩል ደግሞ፣ ሰውየው ወደ ንስሓ ይደርስ ዘንድ ሥጋውን እንዲያጕሳቍል ለሰይጣን ፈቃድ አሳልፎ መስጠትን ያመለክታል። *መንፈሱ ... ትድን ዘንድ፤* ከ3፥15 ጋር ያነጻጽሩ። ከቤተ ክርስቲያን የሚወገደው ሰው ክርስቲያን ሊሆን ይችላል። *በጌታ ቀን፤* ክርስቶስ ዳግም በሚመለስበት ዕለት ማለት ነው (1፥7 ይመ)። *እንደዚህ ዐይነቱ ለሰይጣን ይሰጥ፤* ዲያቢሎስ እንደ ልቡ እንዲያሠቃየው፣ በደለኛውን ሰው አሳልፋችሁ ስጡት ማለቱ ነው። በደለኛው ለሰይጣን ዐልፎ የሚሰጠው በአስማት ወይም በመተት ሳይሆን፣ ከቤተ ክርስቲያን እንዲወገድ በማድረግ ነው (ቍ 13፤ እንዲሁም ቍ 2:7:11 ይመ)። ከቤተ ክርስቲያን ማስወገድ ማለት፣ ከእግዚአብሔር ሕዝብ ተለይቶ ክፉኛ እንዲቀጣ ወደ ሰይጣን ግዛት መስደድ ማለት ነው።

5፥6 *ጥቂት እርሾ ብዙውን ሊጥ፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ ክርስቲያንኖች በቅድስናና በሥርዐት መኖር እንዳለባቸው በሚገባ ለመግለጽ፣ እስራኤላውያን የፋሲካን በዓል ሲያከብሩ እርሾ ያለበትን እንጀራ እንዳይበሉ የሚከለክለውን ሕግ ይጠቅሳል(ዘፀ 12፥15 ይመ)። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ብዙውን ጊዜ እርሾ የክፋት ወይም የኀጢአት ምሳሌ ነው (የማር 8፥15 ማብ ይመ)፤ እዚህ ላይ ቤተ ክርስቲያን የኀጢአትን እርሾ እንድታስወግድ (ቍ 8) ምክር ተሰጥቶአታል፤ ምክንያቱም አንድ ክርስቲያን በክርስቶስ አዲስ ፍጥረት በሆነ ጊዜ እርሾ ያልገባበት ሊጥ ነው (2ቆሮ 5፥17)።

5፥7 *አሮጌውን እርሾ አስወግዱ፤* እስራኤላውያን የፋሲካን እራት ከማዘጋጀታቸው በፊት፣ እርሾ የገባበትን የእንጀራ ፍርፋሪ ሁሉ ከየቤታቸው ጠራርገው ያስወግዱ የነበረውን ልማድ ሳያመለክት አይቀርም። *አሁን ያለ እርሾ እንደ ሆናችሁ ሁሉ፤* አማኞች አዲስ ፍጥረት በመሆናቸው በእግዚአብሔር ፊት የተቀደሱ ናቸው (1፥2፤ 6፥11 ይመ)፤ ነገር ግን ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚያሳስባቸው በዕለት ተዕለት ኑሮአቸውም ቅዱሳን እንዲሆኑ ነው (የ1፥2 ማብ ይመ)። *የፋሲካ በጋችን የሆነ ክርስቶስ፤* አይሁድ ይሠውት የነበረው የፋሲካ በግ እውነተኛውን ትርጒም ያገኘው፣ ክርስቶስ በመስቀል ላይ በሞተ ጊዜ ነው (ኢሳ 53፥7፤ ዮሐ 1፥29)፤ የእግዚአብሔር በግ የሆነው ክርስቶስ የተሰቀለው በዕለተ ፋሲካ ነው፤ ይህም በዓል መከበር የሚጀምረው የፋሲካ እራት ከመበላቱ በፊት አንድ ቀን አስቀድሞ ባለው ምሽት ላይ ነው (ከዘፀ 12፥8 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥8 *በዓሉን ... እናክብር፤* ከፋሲካ በኋላ የሚከበረው ይህ የቂጣ በዓል በምሳሌነት የሚያመለክተው፣ ክርስቲያኖች ሕይወታቸውን በቅድስና ለእግዚአብሔር ማስገዛት እንዳለባቸው ነው (ከሮሜ 12፥1-2፤ 1ጴጥ 2፥5 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ደግሞም ከግፍና ከክፋት እንዲሁም የሥጋ ዝምድና ባላቸው ሰዎች መካከል ከሚፈጸም ጋብቻ መራቅ አለባቸው።

5፥9 *በመልእክቴ ጽፌላችሁ ነበር፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚያብራራው፣ ከዚህ በፊት መልእክቱ ላይ የጠቀሰውን ሐሳብ ነው፤ ይህ መልእክት ግን ደብዛው አልተገኘም። የቆሮንቶስ ሰዎች ከኀጢአት መለየት ሲባል፣ አማኝ ያልሆኑ ሰዎችን ጨምሮ ኀጢአተኛ ከሆኑ ሰዎች ሁሉ መለየት ስለመሰላቸው መልእክቱን በትክክል አልተረዱትም ነበር። ነገር ግን ጳውሎስ እንዲለዩ የፈለገው ክርስቲያን ወንድሞች ነን እያሉ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ኀጢአት ከሚሠሩ ሰዎች ነበር (ቍ 10-11)።

5፥11 *ከእንደዚህ ዐይነቱ ሰው ጋር ምግብ እንኳ አትብሉ፤* አንድ ሰው በኀጢአት እየተመላለሰ ክርስቲያን ነኝ ቢል ይነቀፋል፤ ውርደትም ላይ ይወድቃል፤ ስለ ክርስቶስም የሚሰጠው ምስክርነት ሐሰተኛ ነው። እውነተኛ ክርስቲያን እንደዚህ ካለ ሰው ጋር የጠበቀ ግንኙነት ካደረገ፣ ቤተ ክርስቲያንን ከማስ ወቀሱም በላይ የሚያምኑ ሰዎች ቤተ ክርስቲያን እንዲህ ያለውን ርኵሰትና ቅድስና የጐደለው ሕይወት የተቀበለች ሊመስላቸው ይችላል፤ ከዚህም የተነሣ የክርስቶስ ስም ይነቀፋል፤ የእውነተኛ ክርስቲያኖችም ምስክርነት ጥያቄ ውስጥ ሊገባ ይችላል (ከሮሜ 16፥17-18፤ 2ተሰ 3፥6፤ 14-15 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥12 *በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ባሉት ሰዎች ላይ እናንተ አትፈርዱምን?* ቤተ ክርስቲያን ምእመናን የመገሠጽና የመቅጣት ኀላፊነት አለባት (ከማቴ 18፥15-18 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ነገር ግን ባላመነው ዓለም ላይ የመፍረድ መብት የላትም፤ በዓለም ላይ የመፍረድ ሥልጣን ያላቸው ገዦች አሉ (ሮሜ 13፥1-5)፣ በመጨረሻም በመላው ዓለም ላይ የሚፈርድ እግዚአብሔር ነው (ቍ 13፤ ከራእ 20፥11-15 ጋር ያነጻጽሩ)።

6፥1 *አንድ ሰው ከሌላው ጋር ሙግት ቢኖረው፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚናገረው ስለ ወንጀል ነክ ጉዳዮች ሳይሆን ስለ ልዩ ልዩ የፍትሐ ብሔር ክሶች ነው፤ በቍ 7 ላይ፣ "ብትታለሉስ አይሻልምን?" የሚለው ሐረግ ከዚህ ጋር ሲነጻጸር፣ ጳውሎስ ያተኰረው በመንግሥት ደረጃ ሊታይ ስለሚገባው ወንጀል እንዳልሆነ ግልጽ ነው (ሮሜ 13፥3-4)። *በቅዱሳን ፊት፤* የቆሮንቶስ ሰዎች

በማቅረብ ፈንታ እንዴት ደፍሮ በማያምኑ ሰዎች ፊት ለመፋረድ ያቀርባል? [2]ቅዱሳን በዓለም ላይ እንደሚፈርዱ አታውቁምን? በዓለም ላይ የምትፈርዱ ከሆነ፣ እንግዲያው፣ በትንሹ ነገር ላይ ለመፍረድ አትበቁምን? [3]በምድራዊ ሕይወት ጉዳይ ቀርቶ፣ በመላእክት ላይ እንኳ እንደምንፈርድ አታውቁምን? [4]እንግዲህ እንዲህ ያለ ጉዳይ ሲያጋጥማችሁ፣ በቤተ ክርስቲያን የተናቁን ሰዎች ፈራጅ አድርጋችሁ ሹሟ^! [5]ይህንንም የምለው ላሳፍራችሁ ብዬ ነው። ለመሆኑ ከመካከላችሁ ወንድሞችን ለማስታረቅ የሚበቃ አስተዋይ ሰው የለምን? [6]ነገር ግን ወንድም ወንድሙን ለመክሰስ ፍርድ ቤት ይሄዳል፤ ያውም በማያምኑ ሰዎች ፊት!

[7]እንግዲህ በመካከላችሁ መካሰስ መኖሩ ራሱ ውድቀታችሁን ያሳያል። ብትበደሉ አይሻልምን? ብትታለሉስ አይሻልምን? [8]እናንተ ግን ራሳችሁ ትበድላላችሁ፤ ታታልላላችሁም፤ ያውም ወንድሞቻችሁን።

[9]ዐመፀኞች የእግዚአብሔርን መንግሥት እንደማይወርሱ አታውቁምን? በዚህ ነገር አትታለሉ፤ ሴሰኞች፣ ጣዖት አምላኪዎች፣ አመንዝሮች፣ ወንደቃዎች፣ ግብረ ሰዶማውያን፣ [10]ወይም ሌቦች፣ ስግብግቦች፣ ሰካራሞች፣ ተሳዳቢዎችና ቀማኞች የእግዚአብሔርን መንግሥት አይወርሱም። [11]ከእናንተ አንዳንዶቻችሁ እንደ ዚህ ነበራችሁ፤ አሁን ግን በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ስምና፣ በአምላካችን መንፈስ ታጥባችኋል፤ ተቀድሳችኋል፤ ጸድቃችኋል።

6፥2 ማቴ19፥28፤ ሉቃ22፥30፤1ቆሮ5፥12
6፥5 ሐሥ1፥15፤ 1ቆሮ4፥14
6፥6 ሮሜ7፥1፤ 2ቆሮ6፥14፡15፤ 1ጢሞ5፥8
6፥7 ማቴ5፥39፡40
6፥8 1ተሰ4፥6
6፥9 ዘሌ18፥20፡22፤ዘዳ22፥22፤ ኢዮ13፥9፤ማቴ25፥34፤1ቆሮ15፥33፤ ገላ6፥7፤ያዕ1፥16
6፥10 1ጢሞ1፥10፤ ራእ21፥8፤22፥15
6፥11 ሐሥ22፥16፤ ሮሜ4፥25፤ 1ቆሮ1፥2፤ኤፌ2፥2
6፥12 1ቆሮ10፥23
6፥13 ቆላ15፡19፤ ሮሜ12፥1፤ቈላ2፥22
6፥14 ሐሥ2፥24፤ ሮሜ6፥5፤ኤፌ1፥19፡20፤1ተሰ4፥16
6፥15 ሮሜ12፥5
6፥16 ዘፍ2፥24፤ ማቴ19፥5፤ኤፌ5፥31
6፥17 ዮሐ17፥21-23፤ሮሜ8፥9-11፤ ገላ2፥20

## የዝሙት ኀጢአት

[12]"ሁሉ ነገር ተፈቅዶልኛል፤" ይሁን እንጂ ሁሉም ነገር አይጠቅምም፤ "ሁሉ ነገር ተፈቅዶልኛል፤" ይሁን እንጂ ምንም ነገር በእኔ ላይ አይሠለጥንም። [13]ደግሞም፣ "ምግብ ለሆድ ነው፤ ሆድም ለምግብ ነው፤" እግዚአብሔር ግን ሁለቱንም ያጠፋቸዋል። ሰውነት ለጌታ ነው እንጂ ለዝሙት አይደለም፤ ጌታም ለሰውነት ነው። [14]እግዚአብሔር ጌታን ከሙታን እንዳስነሣው፣ እኛንም ደግሞ በኀይሉ ከሙታን ያስነሣናል። [15]ሰውነታችሁ የክርስቶስ የአካሉ ብልቶች እንደ ሆነ አታውቁምን? ታዲያ፣ የክርስቶስን ብልቶች ወስጄ ከዝሙት አዳሪ ብልቶች ጋር አንድ ላድርገውን? ከቶ አይገባም! [16]ወይስ ከዝሙት አዳሪ ጋር የሚተባበር ሰው ከእርስዋ ጋር አንድ ሥጋ እንደሚሆን አታውቁምን? "ሁለቱ አንድ ሥጋ ይሆናሉ" ተብሎአልና። [17]ነገር ግን ከጌታ ጋር የሚተባበር ከእርሱ ጋር አንድ መንፈስ ይሆናል።

*^4 ወይም በቤተ ክርስቲያን የተናቁ ሰዎችን ፈራጅ አድርጋችሁ ትሾማላችሁ?*

በንብረት ጉዳይ ሙግት ቢያጋጥማቸው፣ ሁኔታውን ለመዳኘት ብቃት ወዳላቸው ክርስቲያኖች መውሰድ አለባቸው። በጳውሎስ በነበረበት ዘመን የንብረት ጉዳይን በተመለከተ፣ አይሁድ በራሳቸው ሕግ እንዲተዳደሩ ሮማውያን ፈቃድ ሰጥተዋቸው ነበር፤ ሮማውያን በዚህ ጊዜ ክርስቲያኖችን ገና ከአይሁድ ለይተው ስላላዩአቸው፣ ክርስቲያኖችም ከአይሁድ ጋር ተመሳሳይ መብት እንደነበራቸው ጥርጥር የለውም።

6፥2 *ቅዱሳን በዓለም ላይ እንደሚፈርዱ፤* የሚፈርዱት ከክርስቶስ ጋር ነው ከማቴ 19፥28፤ 2ጢሞ 2፥12፤ ራእ 20፥4 ጋር ያነጻጽሩ። *በትንሹ ነገር ላይ ለመፍረድ አትበቁምን?* ክርስቲያኖች ነገሮችን ሁሉ ከእግዚአብሔር አንጻር ስለሚመለከቱ፣ በመካከላቸው አለመግባባት ቢፈጠር ዳኝነት ለመስጠት ብቃት እንዳላቸው ጳውሎስ ይናገራል። ክርስቲያኖች ወደ ፊት በዓለምና በመላእክት ላይ ከሚሰጡት ፍርድ ጋር ሲነጻጸር፣ በምድራዊ ሕይወት ጉዳይ የሚሰጡ ፍርድ ከቍጥር አይገባም።

6፥3 *በመላእክት ላይ እንኳ እንደምንፈርድ፤* ከ2ጴጥ 2፥4፡9፤ ይሁ 6 ጋር ያነጻጽሩ።

6፥4 *የተናቁ ሰዎች፤* ይህን ሐረግ በሁለት መልክ ማየት ይቻላል፤ ይህ ሐረግ በቤተ ክርስቲያን ከሚገኙ ምእመናን መካከል፣ እጅግ አነስተኛ ችሎታ ያላቸው ምእመናን እንኳ፣ እንደዚህ ያለውን ተራ ነገር መዳኘት እንደሚችሉ፤ ወይም በአማኞች መካከል የሚነሣውን አለመግባባት እንዲዳኙ ብቃት ወደሌላቸው አረማውያን ዳኞች ጉዳያቸውን ለማቅረብ መሄድ እንዳለባቸው በምፀት መጠየቁን ያመለክታል።

6፥7 *ውድቀታችሁን ያሳያል፤* የቆሮንቶስ ሰዎች እንዲህ የተባሉት ልግስናን፣ ይቅርታንና ፍቅርን በመለማመድና ከዚህም አልፈው ተርፈው ስለ ሌላው ሰው በመጐዳት ፈንታ ስግብግቦች፣ ቂመኞችና በጥላቻ የተሞሉ በመሆናቸው ሊሆን ይችላል።

6፥9 *የእግዚአብሔርን መንግሥት እንደማይወርሱ፤* ከዮሐ3፥3-5 ያነጻጽሩ። *ሴሰኞች፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ ስለ ሦስት ዐይነት ሴሰኝነት ለይቶ ይናገራል፤ ይኸውም ስለ አመንዝሮች፣ ስለ ወንደቃዎችና ስለ ግብረ ሰዶማውያን ነው። በሮሜ 1፥26 ላይ ግብረ ሰዶማውያኑ ሴቶች እንዳሉም ይናገራል። የዚህ ዐይነቱን ተግባር የሚፈጽሙና በቍ 9-10 ላይ የተዘረዘሩት ዐመፀኞች በእግዚአብሔር መንግሥት ስፍራ እንደሌላቸው በግልጽ ተመልክቷል (ሆኖም ከዚህ ቀጥሎ ያለውን ማጥኛ ጽሑፍ ይመ)።

6፥11 *ከእናንተ አንዳንዶቻችሁ እንደዚህ ነበራችሁ፤ አሁን ግን፤* ይሁን እንጂ እግዚአብሔር በቍ 9-10 ላይ የተዘረዘሩትን ዐይነት ሰዎች ያድናል፤ ይቀድሳል።

6፥12 *ሁሉ ነገር ተፈቅዶልኛል፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚጠቅሰው፣ እንዳሻን የመኖር መብት አለን እያሉ ዐጕል የሚንቀባረሩትን የአንዳንድ የቆሮንቶስ ክርስቲያኖችን ብሂል ሳይሆን አይቀርም። ሐዋርያው ግን እንዲህ ያለው "ነጻነት" ለክርስቲያኖች ጥቅም ቢስ እንደ ሆነ ብሂሉን በማስተባበል ይቃወማል። ምንም ነገር በእኔ ላይ አይሠለጥንም፤ በ "ነጻነት" ስም የሚደረግ ነገር ሁሉ መልሶ ባሪያ ሊያደርግ ይችላል (የ10፥23 ማብ ይመ)።

6፥13 *ምግብ ለሆድ ነው፤ ሆድም ለምግብ ነው፤* እዚህም ላይ ጳውሎስ የሚጠቅሰው የምንበላው ምግብ ሁሉ በመንፈሳዊ ሕይወት ላይ የሚያመጣው ለውጥ እንደሌለው ሁሉ፣ አለገደብ የሚደረግ የግብረ ሥጋ ግንኙነትም በመንፈሳዊ ሕይወት ላይ የሚያስከትለው ጕዳት የለም የሚሉትን አንዳንድ የቆሮንቶስ ሰዎች ሊሆን ይችላል። *ሰውነት ለጌታ ነው እንጂ ለዝሙት አይደለም፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ የሰው አካል ምን ያህል ክቡር መሆኑን ይገልጻል፤ አካል የተፈጠረው ለጌታ ነውና። ምግብና ሆድ ዐላፊ ጠፊ ቢሆኑም፣ ማንም በሰውነቱ ላይ የፈለገውን ቢያደርግ ምንም አይደለም የሚለውን ሐሳብ ጳውሎስ አይቀበልም። ይህም በተለይ እግዚአብሔር ለሰው ልጅ ባዘጋጀቸው ጋብቻ ውስጥ የሚፈጸመውን ሩካቤ ሥጋ ይመለከታል (ከዕብ 13፥14 ጋር ያነጻጽሩ)።

6፥14 *እግዚአብሔር ጌታን እንዳስነሣው፣ ... እኛንም ... ያስነሣናል፤* እግዚአብሔር ለሰው አካል ግድ ያለው መሆኑን ለማሳየት፣ እዚህ ላይ ጳውሎስ የጌታን ትንሣኤና በኋላም የሚሆነውን የአማኞችን ትንሣኤ ለአብነት ይጠቅሳል (15፥51-53፤ 1ተሰ 4፥16-17)። ትንሣኤ የሚያገኝ አካል፣ ለርኩሰት መዋል የለበትም።

6፥15 *የክርስቶስ የአካሉ ብልቶች፤* 12፥27 ይመ። የክርስቶስ የአካሉ ብልት የሆነው የሰው መንፈስ ብቻ ሳይሆን፣ መንፈስንና ሥጋን በአንድነት የያዘው መላ ሰብእናው ነው። የሰው አካል ክቡር መሆኑን የሚያረጋግጠውም ይኸው ነው።

6፥16 *ከእርስዋ ጋር አንድ ሥጋ እንደሚሆን፤* በሩካቤ ሥጋ ጊዜ ሁለቱ አንድ ይሆናሉ (ከዘፍ 2፥24፤ ማቴ 19፥5 ጋር ያነጻጽሩ)። ከጋብቻ ውጭ የሚፈጸም ሩካቤ ሥጋ አምላክ የደነገገውን ጋብቻ በእጅጉ የሚቃረን ተግባር ነው።

6፥17 *ከእርሱ ጋር አንድ መንፈስ ይሆናል፤* ከጋብቻ የላቀ ሌላ አንድነት አለ ማለት ነው፤ ይኸውም በአማኞችና በክርስቶስ መካከል ያለ መንፈሳዊ አንድነት ነው፤ ይህም በጋብቻ ውስጥ ሊኖር ስለሚገባው አንድነት ፍጹም ምሳሌ ነው (ከኤፌ

[18]ከዝሙት ሽሹ:: ሰው የሚሠራው ኀጢአት ሁሉ ከአካሉ ውጭ ነው፤ ዝሙትን የሚፈጽም ግን በገዛ አካሉ ላይ ኀጢአት ይሠራል:: [19]ለመሆኑ ሰውነታችሁ በውስጣችሁ የሚኖረው የመንፈስ ቅዱስ ቤተ መቅደስ እንደ ሆነ አታውቁምን? ይህም መንፈስ ከእግዚአብሔር የተቀበላችሁት ነው:: እናንተም የራሳችሁ አይደላችሁም፤ [20]በዋጋ ተገዝታችኋልና፤ ስለዚህ በሰውነታችሁ እግዚአብሔርን አክብሩ::

## ጋብቻን በተመለከተ

**7** ስለ ጻፋችሁልኝ ጉዳይ፣ ሰው ወደ ሴት ባይደርስ መልካም ነው[ሸ]፤ [2]ነገር ግን ከዝሙት ለመጠበቅ፣ እያንዳንዱ ሰው የራሱ ሚስት ትኑረው፤ እያንዳንዷም ሴት የራሷ ባል ይኑራት:: [3]ባል ለሚስቱ የሚገባትን ሁሉ ያድርግላት፤ ሚስትም እንዲሁ ለባሏ የሚገባውን ሁሉ ታድርግለት:: [4]ሚስት አካሏ የራስዋ ብቻ አይደለም፤ የባሏም ነው፤ እንዲሁም ባል አካሉ የራሱ ብቻ አይደለም፣ የሚስቱም ነው:: [5]በጸሎት ለመትጋት ተስማምታችሁ ለተወሰነ ጊዜ ካልሆነ በስተቀር፣ እርስ በርሳችሁ አትከላከሉ፤ ራሳችሁን ባለመግዛት ሰይጣን እንዳይፈታተናችሁ እንደገና አብራችሁ ሁኑ:: [6]ይህን የምለው ግን እንደ ትእዛዝ ሳይሆን እንደ ምክር ነው:: [7]ሰው ሁሉ እንደ እኔ ቢሆን ምኞቴ ነው:: ነገር ግን እያንዳንዱ ሰው ከእግዚአብሔር የተቀበለው የራሱ የሆነ ስጦታ አለው፤ አንዱ አንድ ዐይነት ስጦታ ሲኖረው፣ ሌላው ደግሞ ሌላ ዐይነት ስጦታ አለው::

[8]ላላገቡና ባሎቻቸው ለሞቱባቸው ሴቶች ግን እንዲህ እላለሁ፤ ሳያገቡ እንደ እኔ ቢኖሩ ለእነርሱ መልካም ነው:: [9]ነገር ግን ራሳቸውን መግዛት ካልቻሉ ያግቡ፤ በምኞት ከመቃጠል ማግባት ይሻላልና::

[10]ላገቡት ይህን ትእዛዝ እሰጣለሁ፤ ይህም ትእዛዝ የጌታ እንጂ የእኔ አይደለም:: ሚስት ከባሏ አትለያይ፤ [11]ብትለያይ ግን ሳታገባ ትኑር፤ አለዚያ ከባሏ ጋር ትታረቅ፤ ባልም ሚስቱን አይፍታት::

[12]ለሌሎች ደግሞ እንዲህ እላለሁ፤ ይህንም የምለው እኔ እንጂ ጌታ አይደለም:: ያላመነች ሚስት ያለው ወንድም ቢኖርና ሚስቱ አብራው ለመኖር የምትፈቅድ ከሆነ፣ ሊፈታት አይገባውም:: [13]ያላመነ ባል ያላት ሴት ብትኖርና እርሱም አብሮአት ለመኖር የሚፈቅድ ከሆነ፣ ልትፈታው አይገባትም:: [14]ያላመነ ባል በሚስቱ ተቀድሶአልና፤ ያላመነችም ሚስት በሚያምን ባሏ ተቀድሳለች፤

6፥18 ቍ9፤ ሮሜ6፥12፤1ቆሮ5፥1፤ 2ቆሮ12፥21፤ገላ5፥19፤ ኤፌ5፥3፤1ተሰ4፥3:4፤ ዕብ13፥4
6፥19 ዮሐ2፥21፤ ሮሜ14፥7:8
6፥20 መዝ74፥2፤ ማቴ20፥28፤ሐሥ20፥28፤1ቆሮ7፥23፤ፊል1፥20፤ራእ5፥9፤14፥4
7፥1 ቍ8:26
7፥3 ዘፀ21፥10፤ 1ጴጥ3፥7
7፥5 ዘፀ19፥15፤ 1ሳሙ21፥4:5፤ ማቴ4፥10፤1ተሰ3፥5
7፥6 2ቆሮ8፥8
7፥7 ቍ8፤ ማቴ19፥11:12፤ ሮሜ12፥6፤1ቆሮ9፥5፤ 12፥4:11
7፥8 ቍ1:26
7፥9 1ጢሞ5፥14
7፥10 ሚል2፥14-16፤ሉቃ16፥18
7፥11 ቍ39፤ ሮሜ7፥2:3
7፥12 ቍ6:10፤ 2ቆሮ11፥17
7፥14 ሚል2፥15

*[ሸ]1 ወይም ሰው ከሴት ጋር የግብረ ሥጋ ግንኙነት ባያደርግ መልካም ነው*

5፥21-33 ጋር ያነጻጽሩ)::

6፥18 *ከዝሙት ሽሹ፤* "ሽሹ" ለሚለው የገባው የግሪኩ ቃል፣ የአንድ ጊዜ ድርጊትን ሳይሆን ዘወትር መፈጸም ያለበትን ድርጊት ያመለክታል:: *ሰው የሚሠራው ኀጢአት ሁሉ ከአካሉ ውጭ ነው፤* ምናልባት የዝሙት ርኵሰት የሥጋን ፍላጐት በተለየ መንገድ ያረካ ይሆናል:: *ዝሙትን የሚፈጽም ግን በገዛ አካሉ ላይ ኀጢአት ይሠራል፤* ሰውነታችን የመንፈስ ቅዱስ ቤተ መቅደስ ነው (ቍ 19)፤ በመሆኑም ሰውነታችንን ለአመንዝራነት ማዋል፣ የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ማርከስ ነው:: ከዚህም በላይ የቆሮንቶስ ዝሙት አዳሪዎች የፍቅርና የወሲብ አምላክ ለሆነችው ለአፍሮዲቴ አገልግሎት ራሳቸውን የሰጡ ነበሩ::

6፥19 *ሰውነታችሁ ... የመንፈስ ቅዱስ ቤተ መቅደስ እንደ ሆነ፤* ክርስቲያኖች ሰውነታቸው የተቀደሰ የእግዚአብሔር ማደሪያ መሆኑን መገንዘብ አለባቸው፤ በውስጣቸውም ባደረው በመንፈስ ቅዱስ ህልዎትና ኀይል እንደ ዝሙት ያለው ኀጢአት መቋቋም ይችላሉ (ሮሜ 8፥9):: *የራሳችሁ አይደላችሁም፤* ከ1ጴጥ 2፥9 ጋር ያነጻጽሩ::

6፥20 *በሰውነታችሁ እግዚአብሔርን አክብሩ፤* ከ10፥31፤ ከሮሜ 6፥12-13፤ ቈላ 3፥17 ጋር ያነጻጽሩ::

7፥1 *ስለ ጻፋችሁልኝ ጉዳይ፤* የቆሮንቶስ ሰዎች በርካታ የተቸገሩበት ጉዳይ ስለነበራቸው፣ ጳውሎስን በደብዳቤ ጠይቀውት ነበር (8፥1፤ 12፥1 ይመ):: *ሰው ወደ ሴት ባይደርስ መልካም ነው፤* ይህን የተናገረው በቆሮንቶስ ከነበረው ልቅ የዝሙት ርኵሰት የተነሣ ነው (ቍ 26):: በሌላ ቦታ ግን (ኤፌ 5፥22-33፤ ቈላ 3፥18-19፤ 1ጢሞ 3፥2፡ 12፤ 5፥14) ጋብቻ መልካም እንደ ሆነ ጳውሎስ አበክሮ ይናገራል፤ ደግሞም በ1ጢሞ 4፥1-3 ላይ መጋባትን መከልከል የመጨረሻው ዘመን የክህደት ምልክት እንደሆነ አስተምሮአል:: ሌላው አማራጭ ትርጓሜ ደግሞ እሁንም ጳውሎስ የቆሮንቶስ ሰዎችን ብሂል ጠቅሶ ሊሆን ይችላል (የ6፥12-13፡18 ማብ ይመ):: የሩካቤ ሥጋ ትክክለኛው ስፍራ በጋብቻ ውስጥ እንደሆነ በመግለጽ፣ ይህ ብሂል መሠረት የለሽ መሆኑን በቍ 2 ላይ ያስረዳል::

7፥2 *ከዝሙት ለመጠበቅ፤* በዚያ ዘመን ቆሮንቶስ የዝሙት መዲና እንደ ነበረች ታሪክ ያወሳል፤ ለምሳሌ በቆሮንቶስ አቅራቢያ በሚገኝ ተራራ ላይ አፍሮዲቴ በተባለች እንስት አምላክ ስም የቆመ አንድ ቤተ ጣዖት ነበር፤ በዚህ ቤተ ጣዖት ውስጥ በአንድ ወቅት 1000 የሚደርሱ አመንዝራ እንስት ካህናት ያገለግሉ ነበር::

7፥3 *የሚገባትን ሁሉ ያድርግላት፤* ባልና ሚስት ተገቢውን ሩካቤ ሥጋ መፈጸም አለባቸው፤ ለረዥም ጊዜ ከሩካቤ ሥጋ መገለል የአንደኛውን ወገን የትዳር ጓደኛ መብት መንፈግ ስለሚሆን ፈተናን ሊጋብዝ ይችላል::

7፥4 *እንዲሁም፤* ባልም ሆነ ሚስት፣ አንዱ የሌላውን ፈቃድ አልፈጽምም ማለት አይችሉም፤ አንዱ በሌላው ላይ ባለመብት ነውና::

7፥5 *እርስ በርሳችሁ አትከላከሉ፤* አንዱ የሌላውን የሩካቤ ሥጋ ፍላጎት ማሟላት አለበት ማለት ነው:: ራሳችሁን ባለመግዛት ሰይጣን እንዳይፈታተናችሁ፤ ባልና ሚስት አማኞች ተገቢውን ግብረ ሥጋ ከመፈጸም ከታቀቡ ሰይጣን በዝሙት ሊፈትናቸው ይችላል:: በሰዎች ውስጥ ያለው የሩካቤ ፍላጎት ብርቱ ነው::

7፥6 *እንደ ትእዛዝ ሳይሆን እንደ ምክር ነው፤* ጋብቻ መልካምና በእግዚአብሔር የተደነገገ ቢሆንም፣ እንደ ቆሮንቶስ ባለ ሁኔታ ውስጥ ግን የግድ አስፈላጊ አልነበረም (ቍ26 ይመ):: በሌላም ሁኔታ (1ጢሞ 5፥14) ጳውሎስ ባሏ የሞተባት ወጣት ሴት እንድታገባ ይመክራል::

7፥10 *ይህን ትእዛዝ እሰጣለሁ፤ ይህም ትእዛዝ የጌታ እንጂ የእኔ አይደለም፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚጠቅሰው ባልና ሚስት ከቶ መፋታት እንደሌለባቸው (ማቴ 5፥32፤ 19፥3-9፤ ማር 1-፥2-12፤ ሉቃ 16፥18) ጌታ ኢየሱስ በምድር ሳለ ያስተማረውን ትምህርት ነው:: ጳውሎስ ይህን የጌታ ትእዛዝ የሰማው ከሌሎች ደቀ መዛሙርት (ገላ 1፥18-19 ጋር ያነጻጽሩ) ወይም በልዩ መገለጥ ከራሱ ከጌታ ኢየሱስ ሊሆን ይችላል::

7፥11 *ብትለያይ ግን ሳታገባ ትኑር፤ አለዚያ ከባሏ ጋር ትታረቅ፤* ጳውሎስ ጌታ ስለ ጋብቻ የሰጠውን ትእዛዝ መሠረት በማድረግ፣ ያገባች ሴት (ወይም ያገባ ወንድ) እንደገና ማግባት እንደሌለባቸው ይናገራል:: ይልቁንም የተለያዩ ወይም የተፋቱ ባልና ሚስት መታረቅ ይኖርባቸዋል:: ከዚህ የምንረዳው ባልና ሚስት ተለያይተው መቅረት እንደሌለባቸው ነው::

7፥12 *እንዲህ እላለሁ፤ ይህንም የምለው እኔ እንጂ ጌታ አይደለም፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የጠቀሰው በቀጥታ ከጌታ የተሰጠውን ትእዛዝ አይደለም:: *ያላመነች ሚስት ያለው ወንድም ቢኖር፤* ሐዋርያው እዚህ ላይ (እንዲሁም በቍ 13 ላይ) የሚናገረው፣ ቀድሞ ስለ ተጋቡ ባልና ሚስት ሲሆን ከሁለት አንዱ ቢያምንና ያላመነው ወገን አብሮ በመኖሩ ካልተቃወመ አብረው መኖር አለባቸው (ቍ 15)::

7፥14 *ያላመነ ባል በሚስቱ ተቀድሶአልና፤ ያላመነችም ሚስት በሚያምን ባሏ ተቀድሳለች፤* ያላመነው የትዳር ጓደኛ አማኝ በሆነው የትዳር ጓደኛ የተቀደሰ ሕይወት ወደ ማመን ይሳባል፤ ስለዚህ ይህ ቤተ ሰብ በአማኙ የተቀደሰ ሕይወት ወደ ማመን

አለዚያማ ልጆቻችሁ ርኵሳን በሆኑ ነበር፤ አሁን ግን የተቀደሱ ናቸው::

[15]ነገር ግን የማያምነው ወገን መለየት ከፈለገ ይለይ፤ አንድ ወንድም ወይም እኅት በዚህ ሁኔታ የታሰሩ አይደሉም፤ እግዚአብሔር የጠራን በሰላም እንድንኖር ነው:: [16]አንቺ ሴት፤ ባልሽን ታድኚው እንደ ሆነ ምን ታውቂያ ለሽ? ወይስ አንተ ሰው፤ ሚስትህን ታድናት እንደ ሆነ ምን ታውቃለህ?

[17]ብቻ እያንዳንዱ ሰው ጌታ እንደ ወሰነለት፣ እያንዳንዱም እግዚአብሔር እንደ ጠራው በዚያው ይመላለስ:: በአብያተ ክርስቲያናትም ሁሉ የም ንደነግገው ይህንኑ ነው:: [18]አንድ ሰው ተገርዞ ሳለ ቢጠራ፣ እንዳልተገረዘ ሰው አይሁን፤ ሳይገረዝም ተጠርቶ ከሆነ አይገረዝ:: [19]መገ ረዝም ሆነ አለመገረዝ አይጠቅምም፤ ዋናው ነገር የእግዚአብሔርን ትእዛዝ መፈጸሙ ነው:: [20]እያንዳንዱ ሰው በተጠራበት ሁኔታ ጸንቶ ይኑር:: [21]በተጠራህ ጊዜ ባሪያ ነበርህን? በዚህ አትጨነቅ፤ ነጻነትህን ማግኘት ከቻልህ ግን ነጻነትህን ተቀበል:: [22]ምክንያቱም ባሪያ ሆኖ ሳለ በጌታ የተጠራ፣ የጌታ ነጻ ሰው ነው፤ እንዲሁም ሲጠራ ነጻ የነበረ ሰው የክርስቶስ ባሪያ ነው:: [23]በዋጋ ተገዝታችኋል፤ ስለዚህ የሰው ባሪያ አትሁኑ:: [24]ወንድሞች ሆይ፤ እያንዳንዱ ሰው በተጠራበት ሁኔታ ከእግዚ አብሔር ጋር ጸንቶ ይኑር::

[25]ስለ ደናግል፣ ከጌታ የተቀበልሁት ትእ ዛዝ የለኝም፤ ይሁን እንጂ ከጌታ ምሕረት የተነሣ እንደ ታማኝ ሰው፣ ምክሬን እሰጣ ለሁ:: [26]አሁን ካለው ችግር የተነሣ ባላችሁ በት ሁኔታ ብትኖሩ መልካም ይመስለኛል:: [27]አግብተህ ከሆነ መፋታትን አትሻ፤ ካላገባ ህም ሚስት ለማግባት አትፈልግ:: [28]ብታገባ ግን ኀጢአት አልሠራህም፤ ድንግሊቱም ብታ ገባ ኀጢአት አላደረገችም:: ነገር ግን የሚ ያገቡ ሰዎች በዚህ ዓለም ብዙ ችግር ይገጥማ ቸዋል፤ እኔም ይህ እንዳይደርስባችሁ እወዳለሁ::

[29]ወንድሞች ሆይ፤ ሐሳቤ እንዲህ ነው፤ ዘመኑ አጭር ነው፤ ከእንግዲህ ሚስት ያላቸው እንደሌላቸው ሆነው ይኑሩ:: [30]የሚያለቅሱ እንደማያለቅሱ፣ ደስተኞች ደስ እንደማይላቸው ይሁኑ፤ ዕቃ የሚገዙም የገዙት ነገር የእነ ርሱ እንዳልሆነ ይቍጠሩ፤ [31]በዚህ ዓለም ነገር የሚጠቀሙም እንደማይጠቀሙበት ይሁኑ፤ የዚህ ዓለም መልክ ዐላፊ ነውና::

[32]እኔስ ያለ ጭንቀት እንድትኖሩ እወዳለሁ:: ያላገባ ሰው ጌታን ደስ ለማሰኘት ስለ ጌታ ነገር ያስባል፤ [33]ያገባ ሰው ግን ሚስቱን ደስ ለማሰኘት የዚህን ዓለም ነገር ያስባል፤ [34]በዚህም ልቡ ተከፍሎአል:: ያላገባች ሴት ወይም ድንግል ስለ ጌታ ነገር ታስባለች፤ ዓላ ማዋም በሥጋና በመንፈስ ለጌታ መቀደስ ነው:: ያገባች ሴት ግን ባሏን ደስ ለማሰ ኘት የዚህን ዓለም ነገር ታስባለች:: [35]ይህ ንም የምለው ለእናንተ የሚበጃችሁን ነገር በማ

7፥15 ሮሜ14፥19፤ 1ቆሮ14፥33
7፥16 ሮሜ11፥14፤ 1ጴጥ3፥1
7፥17 ሮሜ12፥3፤ 1ቆሮ4፥17፤14፥33፤ 2ቆሮ8፥18፤11፥28
7፥18 ሐሥ15፥1-2
7፥19 ሮሜ2፥25-27፤ ገላ5፥6፤6፥15፤ ቈላ3፥11
7፥20 ቍ24
7፥22 ዮሐ8፥32፡36፤ ሮሜ6፥22
7፥23 1ቆሮ6፥20
7፥24 ቍ20
7፥25 ቍ6፤ 2ቆሮ8፥8፤2ቆሮ4፥1፤ 1ጢሞ1፥13፡16
7፥26 ቍ1፡8
7፥27 ቍ20፡21
7፥28 ቍ36
7፥29 ቍ31፤ ሮሜ13፥11፡12
7፥31 ቍ29፤ ዕብ12፥27
7፥32 1ጢሞ5፥5
7፥34 ሉቃ2፥37
7፥35 መዝ86፥11

ስለሚሳብ ይቀደሳል የተባለው በዚህ ምክንያት ነው:: *ልጆቻችሁ ... የተቀደሱ ናቸው፤* የሚቀደሱት ቢያንስ በአንደኛው አማኝ ወላጅ በኩል በቅድስና ሕይወት ድባብ ሥር የማደግ ዕድል ስለሚኖራ ቸው ነው (ቍ 16 ይመ):: አንዳንድ ሰዎች እነዚህ ልጆች ቅዱሳን የተባሉት፣ የአብርሃም ልጆች ለአባታቸው በተገባው ኪዳን ውስጥ እንደተጠቃለሉ (በግዝረት) ሁሉ፣ በክርስቶስ በተገኘው አዲሱ ኪዳን ውስጥ ከወላጆቻቸው ጋር በመጠቃለላቸው ነው ይላሉ::

7፥15 *አንድ ወንድም ወይም እኅት በዚህ ሁኔታ የታሰሩ አይደሉም፤* አንድ ክርስቲያን የማያምን የትዳር ጓደኛው አብሮት ለመኖር ካልፈለገ፣ አልፈልግም ካለው ሰው ጋር የመኖር ግዴታ የለበትም:: *በሰላም እንድንኖር፣* የማያምን ከሚያምን ጋር እንዲ ኖር ቢገደድ በቤት ውስጥ ሰላም ሊኖር አይችልም::

7፥17 *ጌታ እንደ ወሰነለት፣ ... በዚያው ይመላለስ፤* እያንዳንዱ ክርስቲያን ባለበት ስፍራና ሁኔታ ረክቶ ለጌታ መኖር አለበት፤ ለምሳሌ ቍ 18 ይመ::

7፥18 *ተገርዞ ሳለ ... ሳይገረዝም፤* ክርስቲያን የሆነ አይሁድ ቀደም ሲል ስለ ተገረዘ አይጸጸት፤ ክርስትናን የተቀበለ አሕዛብም እንደ አይሁድ ለምን አልተገረዝሁም ብሎ አይቈጭ ማለት ነው (ከሐሥ 15፥1-5፤ ገላ 5፥1-3 *ጋር ያነጻጽሩ*)::

7፥19 *የእግዚአብሔርን ትእዛዝ መፈጸሙ፤* ይህን የተናገረው ድነት በእምነት የሚገኝ መሆኑን ያስተማረው (ሮሜ 3-4) ራሱ ጳውሎስ ነው:: ስለዚህ አንዱ ዐቢይ ጕዳይ የእግዚ አብሔርን ትእዛዝ አክብሮ መገኘት ነው፤ ከእምነት የሆነ ድነትም ወደ መታዘዝ፣ ወደ ፍቅርና ወደ አገልግሎት እንዲያ ደርስ ይጠበቃል:: በአዲስ ኪዳን የተገለጠው ወደ ድነት የሚያ ደርስም እምነት ይኸው ነው (ከገላ 5፥6፤ 6፥15 *ጋር ያነጻጽሩ*)::

7፥21 *ባሪያ ነበርህን?* ክርስቲያን የሆነ ባሪያ በጌታ ነጻ መሆኑን ተረድቶ፣ በየትኛውም የኑሮ ደረጃ ላይ ቢሆንም ባለው ነገር ረክቶ ሊኖር ይገባል (ቍ 22፤ ዮሐ 8፥32፡36):: *ነጻነትህን ማግኘት ከቻልህ ግን ነጻነትህን ተቀበል፤* አንድ ክርስቲያን ባሪያ ነጻነቱን የማግኘት ዕድል ካጋጠመው ነጻነትን ባለማወላወል ይቀበል ማለት ነው:: በሮማውያን ዘመን ባሮች አንዳንድ ጊዜ ከአሳዳሪዎቻቸው ነጻነት ይሰጣቸው ነበር:: ያለህበትን ሁኔታ ለማ ሻሻል ያለህ ፍላጎት ምንም ክፋት የለበትም፤ ነገር ግን በደረስህ በት ደረጃ ሁሉ ርካታ ይኑርህ::

7፥22 *ሲጠራ ነጻ የነበረ ሰው የክርስቶስ ባሪያ ነው፤* አንድ ባሪያ ያልሆነ ክርስቲያን በመንፈሳዊው ረገድ የክርስቶስ ባሪያ ነው፤ የክርስቶስ ታማኝ አገልጋይ እንደ መሆኑ መጠን፣ የሚያስተዳድራቸውን ባሪያዎች መጨቈን የለበትም፤ ከኤፌ. 6፥5-9፤ ከቈላ 3፥22፤ 4፥1 *ጋር ያነጻጽሩ*::

7፥23 *በዋጋ ተገዝታችኋል ... የሰው ባሪያ አትሁኑ፤* በየትኛውም የኑሮ ደረጃ የሚገኙ ክርስቲያኖች፣ ከሁሉ በላይ ታማኝነታቸውን ማሳየት ያለባቸው ለሰዎች ሳይሆን፣ በደሙ ለገዛቸው ለክርስቶስ ነው (6፥20፤ 1ጴጥ 1፥18-19)::

7፥25 *ስለ ደናግል፤* ጳውሎስ የቆሮንቶስ ሰዎች ለጠየቁት ሌላ ዐቢይ ጥያቄ መልስ ይሰጣል (ቍ 1):: *እንደ ታማኝ ሰው ምክሬን እሰጣለሁ፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ የሚናገረው በቀጥታ ከጌታ ኢየሱስ የተቀበለውን ትእዛዝ አይደለም (ይህም በቍ 10 ላይ እንደተጻፈው አይደለም፤ ከሐሥ 20፥35 *ጋር ያነጻጽሩ*):: የተነሣው ጕዳይ ትክክል ስለ መሆንና ስላለመሆን ነገር ባይሆንም፣ የጳውሎስ የግሉን አስተያየት ይሰጣል:: ሐዋር ያው ሐሳቡን በዚህ መልክ ቢገልጽም፣ መልእክቱን የጻፈው ግን በመንፈስ ቅዱስ ተመርቶ መሆኑን ከቶ አልተጠራጠረም (ቍ 40 ይመ)፤ የጻፈው በመንፈስ ቅዱስ መሪነት በመሆኑ፣ የሚሰጠው ምክር ሁሉ ቅቡልነቱ አያጠራጥርም::

7፥26 *አሁን ካለው ችግር፣* ርኵሰት በሞላበት በተለይም ክፉ ጠላት በሆነው ዓለም ውስጥ፣ ጭንቅ የበዛበትን የክርስቲያኖች ኑሮ የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (ከቍ 2፡28፤ 5፥11 2ጢሞ 3፥12 *ጋር ያነጻጽሩ*):: ጳውሎስ እዚህ ላይ የሰጠው ምክር በማን ኛውም ጊዜና ሁኔታ ተፈጻሚ የሚሆን አይደለም::

7፥28 *ብዙ ችግር፤* በክርስቶስ ምክንያት መከራና ስደት በሚደርስብን ጊዜ፣ በትዳር ላይ ሆኖ ለትዳር ጓደኛ መጨነቅ፣ ሸክሙን ይበልጥ ያከብደዋል::

7፥29 *ዘመኑ አጭር ነው፤* የጌታን ሥራ የምንሠራበት ጊዜ ከመቼውም ይልቅ እያጠረ መጥቶአል፤ ከመከራ ጊዜ እንደምን ማረው፣ ሕይወት ፈጥና ዐላፊ ናት:: ስለዚህ ለዚህ ዓለም ያለ ልክ መጨነቅ አያስፈልግም (ቍ 29-31)፤ ምክንያቱም በዚህ ዓለም የምናየው ነገር ሁሉ ዐላፊ ጠፊ ነው (ቍ 31):: አንዳንዶች ይህ ሐረግ የጌታን ዳግም ምጽአት ያመለክታል ይላሉ::

7፥34 *ልቡ ተከፍሎአል፤* ሐሳቡ ሳይበታተን በአንድ ልብ ክርስቶስን ማገልገል አይችልም ማለት ነው (ቍ 35)፤ ይህ ደግሞ በስደት ዘመን ይብሳል::

ሰብ እንጂ ላስጨንቃችሁ አይደለም፤ ዓላማዬም ልባችሁ ሳይከፈል በጌታ ጸንታችሁ በአግባብ እንድትኖሩ ነው።

[36]አንድ ሰው ያጫትን ድንግል በአግባቡ ካልያዘ፣ እርሷም በዕድሜ እየገፋች ከሄደች፣ ሊያገባት ካሰበ የወደደውን ያድርግ፤ ኀጢአት የለበትምና ይጋቡ[*]። [37]ነገር ግን በዚህ ጕዳይ ልቡን አረጋግቶ፣ ሳይናወጥ፣ ራሱንም በመግዛት ድንግሊቱን ላለማግባት የወሰነ ሰው መልካም አድርጓል። [38]ስለዚህ ድንግሊቱን ያገባ መልካም አደረገ፤ ያላገባም የተሻለ አደረገ[*]።

[39]አንዲት ሴት ባሏ በሕይወት እስካለ ድረስ ከእርሱ ጋር የታሰረች ናት፤ ባሏ ቢሞት ግን፣ የፈለገችውን ሰው ለማግባት ነጻነት አላት፤ ሰውየው ግን በጌታ መሆን አለበት። [40]እንደ እኔ ከሆን ግን ሳታገባ እንዲሁ ብትኖር ይበልጥ ደስተኛ ትሆናለች፤ እኔም ደግሞ የእግዚአብሔር መንፈስ በእኔ ላይ ያለ ይመስለኛል።

## ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ

**8** ለጣዖት ስለ ተሠዋ ሥጋ ደግሞ ይህን እላለሁ፤ ሁላችንም ዕውቀት እንዳለን እናውቃለን[a]። ዕውቀት ያስታብያል፤ ፍቅር ግን ያንጻል። [2]ዐውቃለሁ የሚል ሰው፣ ማወቅ የሚገባውን ያህል ገና አላወቀም። [3]እግዚአብሔርን የሚወድ ሰው ግን በእግዚአብሔር ዘንድ የታወቀ ነው።

[4]እንግዲህ፣ ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ ስለ መብላት እንዲህ እላለሁ፤ በዚህ ዓለም ጣዖት ከንቱ እንደ ሆነና ከአንዱ ከእግዚአብሔር በስተቀር ሌላ አምላክ እንደሌለ እናውቃለን። [5]መቼም ብዙ አማልክትና ብዙ ጌቶች አሉ፤ በሰማይም ሆነ በምድር አምላክ ተብለው የሚጠሩ አማልክት ቢኖሩም፤ [6]ለእኛ ግን ሁሉም ነገር ከእርሱ የሆነ፣ እኛም ለእርሱ የሆን አንድ አምላክ አብ አለን፤ ደግሞም ሁሉም ነገር በእርሱ አማካይነት የሆነ፣ እኛም በእርሱ አማካይነት የሆን አንድ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ አለን።

[7]ነገር ግን ይህን የሚያውቁ ሁሉም አይደሉም፤ አንዳንድ ሰዎች እስከ አሁን ድረስ ጣዖትን ማምለክ ስለ ለመዱ፣ እንዲህ ያለውን ሥጋ ሲበሉ በእርግጥ ለጣዖት እንደ ተሠዋ ያስባሉ፤ ኅሊናቸውም ደካማ ስለ ሆነ ይረክሳል። [8]ነገር ግን ምግብ ወደ እግዚአብሔር አያቀርበንም፤ ባንበላ የሚጐድልብን ነገር የለም፤ ብንበላም የምናተርፈው ነገር አይኖርም።

[9]ነገር ግን ከነጻነታችሁ የተነሣ የምታደርጉት ለደካሞች ዕንቅፋት እንዳይሆን ተጠንቀቁ።

7፥36 ቍ28
7፥38 ዕብ13፥4
7፥39 ሮሜ7፥2:3፤ 2ቆሮ6፥14
7፥40 ቍ25
8፥1 ቍ4:7:10፤ ሐሥ15፥20፤ ሮሜ15፥14
8፥2 1ቆሮ3፥18፤ 13፥8:9:12፤ 1ጢሞ6፥4
8፥3 ኤር1፥5፤ ሮሜ8፥29፤ገላ4፥9
8፥4 ቍ1:6:7:10፤ ዘፀ34፥15፤ዘዳ6፥4፤ መዝ86፥10፤ ሐሥ14፥15፤ 1ቆሮ10፥19፤ገላ4፥8፤ ኤፌ4፥6፤1ጢሞ2፥5
8፥5 2ተሰ2፥4
8፥6 ቍ4፤ ሚል2፥10፤ዮሐ1፥3፤ ሮሜ11፥36፤ኤፌ4፥5
8፥7 ቍ1፤ ሮሜ14፥14፤ 1ቆሮ10፥28
8፥8 ሮሜ14፥17
8፥9 ሮሜ14፥1፤2 ቆሮ6፥3፤ገላ5፥13

*36-38 *ወይም አንድ ሰው ድንግል የሆነችውን ልጁን በሚገባ እንዳልያዛት ካሰበና እርስዋም በዕድሜ እየገፋች ከሄደች፣ ማግባት እንዳለባት ካሰበ የወደደውን ያድርግ፤ ኀጢአት የለበትምና እንድታገባ ሊፈቅድላት ይገባል። ... 38 ስለዚህ ድንግል የሆነችውን ልጁ ለጋብቻ የሰጠ መልካም አደረገ፤ ለጋብቻ ያልሰጣትም የተሻለ አደረገ።*

a1 *ወይም እናንተ እንደምትሉት* "ሁላችንም ዕውቀት አለን"

7፥36 *ያጫትን ድንግል በአግባቡ ካልያዘ፣ እርሷም በዕድሜ እየገፋች ከሄደች ... ይጋቡ፤* በቆሮንቶስ አማኞች ላይ ከደረሰው ተቃውሞ የተነሣ፣ አንድ ሰው እጮኛውን አለማግባት ይኖርበት ይሆናል፤ ነገር ግን እጮኛው የምታገባበት ዕድሜ እያለፈ የሄደ ከመሰለውና ሁኔታው ለእርሷ ያልተመቾ ሆኖ ከታየው ቢጋቡ እጅግ የተሻለ ነው።

7፥37 *ራሱንም በመግዛት ... መልካም አድርጓል፤* ባለበት ሁኔታ ውስጥ እጮኛውን ላለማግባት የሚወስን ቢኖር መልካም አድርጓል (ቍ 38)። ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚናገረው ስሜቱን መቈጣጠር ስለሚችል ሰው ሳይሆን አይቀርም፤ ይህም በቍ 7 ላይ እንደተመለከተው ነው (ከቍ 9 ጋር ያነጻጽሩ)።

7፥39 *ባሏ በሕይወት እስካለ ድረስ ከእርሱ ጋር የታሰረች ናት፤* ጋብቻ የዕድሜ ልክ ትስስር ነው (ይሁን እንጂ በማቴ 19፥9 ላይ የተሰጠውን ምክንያት ይመ)። *ባሏ ቢሞት ግን፤* የጋብቻ ቃል ኪዳን የሚፈርሰው በሞት ነው፤ በመሆኑም አንድ ክርስቲያን ሌላ ክርስቲያን ማግባት ይችላል ("ሰውየው ግን በጌታ መሆን አለበት")።

7፥40 *ሳታገባ እንዲሁ ብትኖር፤* መበለት ሆና ማለት ነው። *እኔም ደግሞ የእግዚአብሔር መንፈስ በእኔ ላይ ያለ ይመስለኛል፤* ጳውሎስ በመንፈስ ቅዱስ እየተመራ እንደሚጽፍ በሙሉ ልብ ይናገራል።

8፥1 *ለጣዖት ስለ ተሠዋ፤* አረማውያን በሚሠዉበት መሠዊያ ላይ የቀረበ ነው። ከመሥዋዕቱ የተረፈውን ሥጋ የጣዖቱ ካህናት፣ መሥዋዕት አቅራቢውና ከእርሱ ጋር ያሉ ሰዎች ይበሉታል (የቍ 10 ማብ ይመ)፤ ወይም ከመሥዋዕቱ የተረፈው ሥጋ በገበያ ይሸጣል። አንዳንድ ክርስቲያኖች በዚህ መልክ የቀረበውን ሥጋ ገዝቶ መብላት፣ ጣዖትን እንደ ማምለክና በክርስቶስ ካላቸው እምነት እንደ ማፈግፈግ ይቈጥሩ ነበር፤ ሌሎች ግን ያን ሥጋ ገዝቶ መብላት ምንም ችግር አያስከትልም ይሉ ነበር። *ስለ ... ሥጋ፤* የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች ለጳውሎስ የጻፉለት ሌላው ጕዳይ ነበር (የ 7፥1 ማብ ይመ)። *ዕውቀት፤* በቍ2-6 ላይ ተብራርቶአል። *ዕውቀት ያስታብያል፤* ያልሆነውን የሆነ እየመሰለው ይኵራራል። *ፍቅር ግን ያንጻል፤* በቍ 7-13 ላይ ተብራርቶአል። አንድ ክርስትያን በእምነቱ ደካማ የሆነ ወንድሙን መውደድ ይገባዋል።

8፥2 *ገና አላወቀም፤* እጅግ አስተዋይና ዐዋቂ ክርስቲያን፣ ዕውቀቱ ውሱን መሆኑን ይረዳል። ሁሉን የሚያውቅ እግዚአብሔር ብቻ ነው (ከሮሜ 11፥33-36 ጋር ያነጻጽሩ)።

8፥3 *እግዚአብሔርን የሚወድ ሰው ግን በእግዚአብሔር ዘንድ የታወቀ ነው፤* ዕውቀቱን በእግዚአብሔር ፍቅር የሚገራ ሰው በእርግጥ በእግዚአብሔር ዘንድ የታወቀ፣ ተቀባይነት ያገኘና የተወደደም መሆኑን ያሳያል (ገላ 48-9፤ 1ዮሐ47-8)።

8፥4 *ጣዖት ከንቱ እንደ ሆነና፤* እንደ እውነቱ ከሆነ አማልክትን አይወክሉም፤ ኀይልም የላቸውም (መዝ 115፥4-7፤ 135፥15-17፤ ኢሳ 44፥12-20 ይመ)፤ ይሁን እንጂ ከጣዖታቱ በስተ ጀርባ አጋንንት አሉ (10፥20)።

8፥5 *አምላክ ተብለው የሚጠሩ፤* በጥንት ግሪካውያንና ሮማውያን ሥነ ተረት ውስጥ የሚታወቁ ናቸው። *ብዙ አማልክትና ብዙ ጌቶች፤* እንዲህ ስለ ተባለ ብዙ አማልክትና ጌቶች አሉ ማለት አይደለም፤ እንዲህማ ቢሆን ኖሮ አንድ አምላክ ብቻ አለ የሚለውን ጽኑ የቅዱሳት መጻሕፍት ትምህርት በተቃረነ ነበር (ዘዳ 6፥4)። እዚህ ላይ ጳውሎስ የሚናገረው በእርግጥ ሕልውና ባይኖራቸውም እንደ አምላክ ተቈጥረው የሚመለኩ ከንቱ አማልክት መኖራቸውን ነው።

8፥6 *ሁሉም ነገር ከእርሱ የሆነ ... ሁሉም ነገር በእርሱ አማካይነት የሆነ፤* ዕብ 2፥10 ይመ። እግዚአብሔር አብ የፍጥረት ሁሉ መገኛ ነው (ሐሥ 4፥24)፤ ሁሉም ነገር ሕልውና ያገኘው በእግዚአብሔር ወልድ አማካይነት ነው (ዮሐ 1፥3፤ ቈላ 1፥16)።

8፥7 *ይህን የሚያውቁ፤* ጣዖት በራሱ ሕልውና እንደሌለው በምንም ዘንድ የታወቀ ነው። *ኅሊናቸውም ደካማ ስለ ሆነ ይረክሳል፤* ጣዖት በራሱ ሕልውና እንዳለው የሚመስላቸው ክርስቲያኖች ራሳቸውን ከዚህ አመለካከት ነጻ ማድረግ አይችሉም፤ ከዚህም የተነሣ አረማውያን በሚሠዉበት መሠዊያ ላይ የቀረበውን ሥጋ በመብላታቸው ጣዖትን እንዳመለኩና ክርስቶስን እንደ በደሉ ይመስላቸዋል።

8፥9 *ከነጻነታችሁ፤* ጣዖት ከንቱ መሆኑን ተረድታችሁ ለጣዖት የተሠዋውን ሥጋ መብላታችሁ (ቍ 4) ማለቱ ነው። *ለደካሞች፤* ለጣዖት የተሠዋውን ሥጋ መብላት ትክክል አይደለም የሚሉት ደካማ ኅሊና ያላቸው ክርስቲያኖች ናቸው።

10አንተ ይህን የመሰለ ዕውቀት ኖሮህ፣ ደካማ ኅሊና ያለው ሰው፣ በቤተ ጣዖት ስትበላ ቢያይህ፣ ለጣዖት የተሠዋውን ምግብ ለመብላት አይደፋፈርምን? 11ስለዚህ ክርስቶስ የሞተለት ይህ ደካማ ወንድም በአንተ ዕውቀት ምክንያት ጠፋ ማለት ነው:: 12በዚህ መንገድ ወንድሞቻችሁን በመበደልና ደካማ ኅሊናቸውን በማቍሰል፣ ክርስቶስን ትበድላላችሁ:: 13ስለዚህ እኔ የምበላው ነገር ወንድሜን የሚያሰናክለው ከሆነ፣ ወንድሜን ላለማሰናከል ስል ከቶ ሥጋ አልበላም::

## የሐዋርያ መብት

**9** እኔ ነጻ ሰው አይደለሁምን? ሐዋርያስ አይደለሁምን? ጌታችንን ኢየሱስን አላየሁትምን? እናንተስ በጌታ የድካሜ ፍሬዎች አይደላችሁምን? 2ለሌሎች ሐዋርያ ባልሆን እንኳ ለእናንተ ግን በእርግጥ ሐዋርያ ነኝ፤ ምክንያቱም በጌታ የሐዋርያነቴ ማኅተም እናንተ ናችሁ::

3ለሚመረምሩኝ የምሰጠው መልስ ይህ ነው:: 4ለመሆኑ፣ የመብላትና የመጠጣት መብት የለንምን? 5እንደ ሌሎቹ ሐዋርያት፣ እንደ ጌታ ወንድሞችና እንደ ኬፋ† ሁሉ፣ እኛስ አማኝ ሚስት ይዘን የመዞር መብት የለንምን? 6ወይስ ጥረን ግረን መኖር ያለብን እኔና በርናባስ ብቻ ነን?

7ለመሆኑ በገዛ ገንዘቡ በወታደርነት የሚያገለግል ማን ነው? ወይን ተክሎ ፍሬውን የማይበላ ማን ነው? መንጋ እየጠበቀ የከብቱን ወተት የማይጠጣ ማን ነው? 8ይህን የምናገረው እንደ ሰው አስተሳሰብ ነውን? የኦሪትስ ሕግ ይህንኑ ይል የለምን? 9በሙሴ ሕግ፣ "የሚያበራየውን በሬ አፉን አትሰር" ተብሎ ተጽፎአልና:: ለመሆኑ፣ እግዚአብሔርን ያሳሰበው የበሬ ጕዳይ ነውን? 10ይህን የተናገረው በእርግጥ ስለ እኛ አይደለምን? የተጻፈው በትክክል ስለ እኛ ነው፤ ዐራሹ የሚያርሰው፣ አበራዩ የሚያበራየው ከምርቱ ድርሻ እንዳለው ተስፋ በማድረግ ነውና:: 11እኛ በእናንተ መካከል መንፈሳዊ ዘር ዘርተን ከሆነ ለሥጋ የሚሆን ነገር ብናጭድ ትልቅ ነገር መሆኑ ነውን? 12ሌሎች ይህን መብት ከእናንተ ማግኘት ከቻሉ፣ እኛ ይበልጥ ማግኘት አይገባንምን?

እኛ ግን በዚህ መብት አልተጠቀምንም፤ ይልቁንም ለክርስቶስ ወንጌል ዕንቅፋት እንዳንሆን ሁሉንም ነገር እንታገሣለን:: 13በቤተ መቅደስ የሚያገለግሉ ምግባቸውን ከቤተ መቅደስ እንደሚያገኙ፣ በመሠዊያውም የሚያገለግሉ ከመሥዋዕቱ እንደሚካፈሉ አታውቁምን? 14እንደዚሁም ወንጌልን የሚሰብኩ ለኑሮ የሚያስፈልጋቸውን ከወንጌል እንዲቀበሉ ጌታ አዞአል::

15እኔ ግን ከእነዚህ መብቶች በአንዱ እንኳ አልተጠቀምሁም፤ አሁንም ይህን የምጽፍላችሁ እንደነዚህ ያሉትን ነገሮች ታደርጉልኛላችሁ በሚል ተስፋ አይደለም፤ ማንም ትምክህቴን ከንቱ ከሚያደርግብኝ ሞት ይሻለኛልና:: 16ወንጌልን መስበኬ አያስመካኝም፤ የምሰብከው ግዴታዬ ስለ ሆነ ነው፤ ወንጌልን ባልሰብክ ግን ወዮልኝ:: 17በፈቃደኝነት ብሰብክ ሽልማት አለኝ፤ በፈቃደኝነት ካልሆነ ግን፣ የምፈጽመው ተግባር የተጣለብኝን ዐደራ

8፥10 ቍ1:4:7
8፥11 ሮሜ14፥15:20
8፥12 ማቴ18፥6፤25፥40:45
8፥13 ማቴ5፥29
9፥1 ቍ19፤ 1ቆሮ1፥1፤3፥6፤4፥15፤15፥8፤2ቆሮ12፥12
9፥2 2ቆሮ3፥2:3
9፥4 ቍ14፤ ሐሥ18፥3
9፥5 ማቴ12፥ 46፤ 1ቆሮ1፥12፤7፥7:8፤
9፥6 ሐሥ4፥36
9፥7 ዘዳ20፥6፤ ምሳ27፥18፤ 1ቆሮ3፥6:8፤ 2ጢሞ2፥3:4
9፥9 ዘዳ22፥1-4፤ 25፥4፤ምሳ12፥10፤ 1ጢሞ5፥18
9፥10 ምሳ11፥25፤ ሮሜ4፥ 23:24፤ 2ጢሞ 2፥6
9፥11 ቍ14፤ ሮሜ15፥27፤ገላ6፥6
9፥12 ቍ15:18፤ ሐሥ18፥3፤2ቆሮ6፥3፤11፥7-12
9፥13 ዘሌ6፥16:26፤ ዘዳ18፥1
9፥14 1ጢሞ5፥18
9፥15 ቍ12:18፤ ሐሥ18፥3፤ 2ቆሮ11፥9:10
9፥16 ሐሥ9፥15፤ 26፥16-18፤ሮሜ1፥14
9፥17 1ቆሮ3፥8፤ 14፤4፥1፤ ገላ2፥7፤ ቆላ1፥25

†5 ጴጥሮስ ማለት ነው

8፥10 *በቤተ ጣዖት ስትበላ፤* የሥነ ቅርስ ተመራማሪዎች የጥንቷ ቆሮንቶስ በነበረችበት ስፍራ ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ የሚበላባቸው ክፍሎች ያሏቸው ሁለት አብያተ ጣዖታት አግኝተዋል:: ክርስቲያኖች ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ ወደሚበላበት ስፍራ በአረማውያን ወዳጆቻቸው ተጋብዘው ሊሆን ይችላል::

8፥11 *ይህ ደካማ ወንድም በአንተ ዕውቀት ምክንያት ጠፋ ማለት ነው፤* አንድ ደካማ ክርስቲያን አድርጎቱ ትክክል አለመሆኑ እየተሰማው፣ ብርቱ በሆነው ክርስቲያን ድርጊት ተስቦ ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ ሊበላ ይችላል:: ይህን ተከትሎ የሚመጣው የመንፈስ መጐዳት በቍ 12 ላይ ተገልጾአል::

8፥12 *ደካማ ኅሊናቸውን በማቍሰል፤* ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ መብላት ትክክል አለመሆኑን እያወቀ መብላት ኅሊናን ሊያደንዝ ይችላል፤ ከዚህም የተነሣ ትክክል ያልሆነውን ነገር ማድረግ እየቀለለ ይመጣል፤ የኋላ ኋላም የሞራል ውድቀት ሊያስከትል ይችላል:: *ክርስቶስን ትበድላላችሁ፤* ክርስቶስ ለእናንተ እንደ ሞተ ሁሉ ለወንድማችሁም ሞቶአል (ቍ 11):: እንዲሁም ክርስቶስን መበደል ነው፤ ምክንያቱም የአካሉን ብልቶች (የቤተ ክርስቲያንን) አንድነት ያፈርሳል::

8፥13 *ከቶ ሥጋ አልበላም፤* ጳውሎስ ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ መብላት ምንም ጕዳት እንደማያመጣበት ቢያውቅም፣ ደካማ ወንድሙን የሚያሰናክል መስሎ ከታየው ግን ለዘላለም ሥጋ ባይበላ ይመረጣል::

9፥1 *እኔ ነጻ ሰው አይደለሁምን?* እነሱ እንደ ማንኛውም ክርስቲያን መብት የለኝምን? ማለቱ ነው:: *ሐዋርያስ አይደለሁምን?* በቆሮንቶስና (2ቆሮ 12፥11-12) በሌላም ቦታ የነበሩ አንዳንድ ሰዎች (ገላ 1፥1፤ 1፥15-2፥10) የጳውሎስን ሐዋርያነት ተጠራጥረው ነበር:: ጳውሎስ ሐዋርያ መሆኑን ለማረጋገጥ ሌሎች ሐዋርያት ጌታ ኢየሱስን እንዳዩት ሁሉ (ሐሥ 1፥21-22)፣ እርሱም ማየቱን (ሐሥ 9፥ 1-9፤ 22፥6-16፤ 26፥12-18) እንደ ማስረጃ ያቀርባል:: ከዚህም በላይ አገልግሎቱ እውነተኛ መንፈሳዊ ፍሬ (የቆሮንቶስን ሰዎች) ማፍራቱ፣ በእርግጥ ሐዋርያ መሆኑን ሊያሳያቸው እንደሚችል ጨምሮ ይናገራል::

9፥4 *የመብላትና የመጠጣት መብት፤* ጳውሎስና በርናባስ የእግዚአብሔር አገልጋዮች እንደ መሆናቸው መጠን፣ ምግባቸውንና ለኑሮ የሚያስፈልጋቸውን ወጪ ሁሉ ከቤተ ክርስቲያን የማግኘት መብት ነበራቸው (ከቍ 6:13-14 ጋር ያነጻጽሩ)::

9፥5 *አማኝ ሚስት ይዘን፤* ጳውሎስ ቢፈልግ ኖሮ ሚስት የማግባት መብት እንደነበረው ይናገራል:: እንዲህ ሲባል ግን አንዳንዶች እንደሚሉት ጳውሎስ አግብቶ ነበር ማለት አይደለም (7፥7 ይመ):: ጴጥሮስን ጨምሮ ሌሎች ሐዋርያት ግን ሚስቶች ነበሯቸው (ማር 1፥30 ይመ)::

9፥11 *ለሥጋ የሚሆን ነገር፤* የቆሮንቶስ ሰዎች ማዘጋጀት ያባቸውን ምግብ፣ መኝታና ሌላውንም ወጪ ማለት ነው (ከገላ 6፥6 ጋር ያነጻጽሩ):: ጳውሎስ እዚህ ላይ በመርሕ ደረጃ ክርስቲያን አገልጋዮች የድካማቸውን ዋጋ ማግኘት እንዳለባቸው ያስቀምጣል::

9፥12 *በዚህ መብት አልተጠቀምንም፤* ጳውሎስ በም 9 ላይ ያነሳው ርእስ ጕዳይ ነው:: ሐዋርያው የቆሮንቶስ ክርስቲያኖችን ስለሚወዳቸው ብቻ ማንሣት የነበረበት ነገር ግን ያላነሣቸው ብዙ መብቶች ነበሩት:: በመሆኑም በም 8 ላይ ለሌሎች ሲል መብቱን መተው እንደሚገባው የተናገረውን በም 9 ላይ አንዳንድ መብቶቹን ወደ ጐን በመተው የራሱን ሕይወት እንደ ምሳሌ ያቀርባል:: አማኞች ለሌሎች ሲሉ መብታቸውን ለመተው ፈቃደኞች መሆን ይኖርባቸዋል::

9፥13 *በቤተ መቅደስ የሚያገለግሉ፤* የቆሮንቶስ አማኞች ይህን የሚረዱት ከብሉይ ኪዳን ከተማሩት ብቻ ሳይሆን (ከዘሌ 7፥28-36፤ ዘኍ 18፥8-20 ጋር ያነጻጽሩ) በግሪክና በሮም አብያተ ጣዖታትም የተለመደ ነገር በመሆኑ ነው::

9፥15 *ትምክህቴን፤* ትምክህቱ፣ ለአገልግሎቱ ክፍለነዋል እንዳይሉት ወንጌልን በነጻ መስበኩ ነው::

9፥16 *የምሰብከው ግዴታዬ ስለ ሆነ ነው፤* ጳውሎስ ወንጌልን እንዲሰብክ ጌታ ታላቅ ዐደራ ሰጥቶታል (ሐሥ 9፥1-16፤26፥16-18፤ በተጨማሪ ኤር 20፥9 እና ማብ ይመ)::

መወጣት ብቻ ይሆናል:: [18]ታዲያ ሽልማቴ ምንድን ነው? ሽልማቴማ ወንጌልን ስሰብክ በመብቴ ሳልጠቀም ወንጌልን ያለ ክፍያ መስበክ ነው::

[19]እኔ ነጻ ሰው ነኝ፤ የማንም ባሪያ አይደለሁም፤ ነገር ግን ብዙዎችን እመልስ ዘንድ ራሴን ለሰው ሁሉ ባሪያ አደርጋለሁ:: [20]አይሁድን እመልስ ዘንድ ከአይሁድ ጋር እንደ አይሁዳዊ ሆንሁ፤ እኔ ራሴ ከሕግ በታች ሳልሆን፣ ከሕግ በታች ያሉትን እመልስ ዘንድ ከሕግ በታች እንዳሉት ሆንሁ:: [21]እኔ ራሴ ከእግዚአብሔር ሕግ ነጻ ያልሆንሁና፣ ለክርስቶስ ሕግ የምገዛ ብሆንም፣ ሕግ የሌላቸውን እመልስ ዘንድ፣ ሕግ እንደሌለው ሰው ሆንሁ:: [22]ደካሞችን እመልስ ዘንድ፣ ከደካሞች ጋር እንደ ደካማ ሆንሁ:: በሚቻለኝ ሁሉ አንዳንዶችን አድን ዘንድ፣ ከሁሉም ጋር ሁሉን ነገር ሆንሁ:: [23]ይህን ሁሉ የማደርገው፣ ከወንጌል በረከት እካፈል ዘንድ፣ ስለ ወንጌል ብዬ ነው::

[24]በሩጫ ውድድር የሚሮጡ ብዙዎች እንደ ሆኑ፣ ሽልማቱን የሚቀበለው ግን አንዱ ብቻ እንደ ሆነ አታውቁምን? ስለዚህ ሽልማቱን እንደሚቀበል ሰው ሩጡ:: [25]ለውድድር የሚዘጋጅ ማንኛውም ሰው በሁሉም ነገር ራሱን ይገዛል እነርሱ ዐላፊ ጠፊ የሆነውን አክሊል ለማግኘት ይደክማሉ፤ እኛ ግን ለዘላለም የማይጠፋውን አክሊል ለማግኘት እንደክማለን:: [26]ስለዚህ እኔ ግብ እንደሌለው ሰው በከንቱ አልሮጥም፤ ደግሞም ነፋስን እንደ ሚጎስም ሰው እንዲያው አልታገልም፤ [27]ነገር ግን ለሌሎች ከሰበክሁ በኋላ እኔ ራሴ ውድቅ ሆኜ እንዳልቀር፣ ሰውነቴን እየጎሰምሁ እንዲገዛልኝ አደርገዋለሁ::

9፥18 ቊ12:15፤ 2ቆሮ11፥7፤12፥13
9፥19 ቊ1፤ ማቴ18፥15፤ 2ቆሮ4፥5፤ገላ5፥13፤ 1ጴጥ3፥1
9፥20 ሐሥ16፥3፤ 21፥20-26፤ ሮሜ2፥12፤11፥24
9፥21 ሮሜ2፥12:14፤ ገላ6፥2
9፥22 ሮሜ11፥14፤ 14፥1፤1ቆሮ2፥3፤ 10፥33
9፥24 ቊ25:26፤ ገላ2፥2፤5፥7፤ ፊል2፥16፤3፥14፤ ቈላ2፥18፤2ጢሞ4፥7፤ ዕብ12፥1
9፥25 2ጢሞ2፥5፤ 4፥8፤ያዕ1፥12፤ 1ጴጥ5፥4፤ራእ2፥10፤ 3፥11
9፥26 ቊ24፤ 1ጢሞ6፥12
9፥27 ቊ24፤ ሮሜ8፥13
10፥1 ዘፀ13፥21፤ 14፥22:29፤ መዝ66፥6፤105፥39፤ ሮሜ11፥25
10፥2 ሮሜ6፥3
10፥3 ዮሐ6፥31
10፥4 ዘፀ17፥6፤ ዘኍ20፥11፤ መዝ78፥15፤105፥41
10፥5 ዘኍ14፥29፤ ዕብ3፥17፤ይሁ5

## በእስራኤል የደረሰው እንዳይደርስብን እንጠንቀቅ

**10** ወንድሞች ሆይ፤ አባቶቻችን ሁሉ ከደመናው በታች እንደ ነበሩና በባሕሩ ውስጥ እንደ ተሻገሩ ታውቁ ዘንድ እፈልጋለሁ:: [2]እነርሱ ሁሉ ከሙሴ ጋር ለመተባበር በደመናና በባሕር ተጠመቁ:: [3]ሁሉም ከአንድ መንፈሳዊ ምግብ በሉ፤ [4]ሁሉም ከአንድ መንፈሳዊ መጠጥ ጠጡ፤ ይከተላቸው ከነበረው መንፈሳዊ ዐለት ጠጥተዋልና፤ ያ፣ ዐለት ክርስቶስ ነበረ:: [5]ይሁን እንጂ እግዚአብሔር በብዙዎቹ ደስ ስላልተሰኘ በበረሓ ወድቀው ቀሩ::

[6]እነርሱ ክፉ እንደ ተመኙ፣ እኛም ደግሞ እንዳንመኝ እነዚህ ነገሮች ምሳሌ ሆነውልናል:: [7]"ሕዝቡ ሊበሉና ሊጠጡ ተቀመጡ፤ ሊዘፍኑም ተነሡ" ተብሎ እንደ ተጻፈ፣ ከእነርሱ አንዳንዶቹ እንዳደረጉት ጣዖት አምላኪዎች አትሁኑ:: [8]ከእነርሱ አንዳንዶቹ ዝሙት ፈጽመው በአንድ ቀን ሀያ ሦስት ሺህ ሰው እንደ ረገፈ፣ እኛም ዝሙት አንፈጽም::

10፥6 ቊ11 10፥7 ቊ14፤ ዘፀ32፥4:6:19 10፥8 ዘኍ25፥1-9

9፥18 *ሽልማቴ ... ወንጌልን ... መስበክ ነው*፤ የጳውሎስ ሽልማት ምድራዊ ጥቅም ሳይሆን ለቆሮንቶስ ሰዎች ወንጌልን ያለ ክፍያ በመስበክ የሚኖረው ትምክህት ነው፤ ደግሞም ምግብና መጠጥ እንዲሁም መጠለያና ክፍያ የማግኘት መብቱን ሠተው ነው (ቊ 3-12)፡

9፥19 *ራሴን ለሰው ሁሉ ባሪያ አደርጋለሁ፤* ጳውሎስ የተወው ወንጌልን በመስበክ ማግኘት የሚገባውን ምድራዊ ጥቅም ብቻ ሳይሆን፣ ማኅበራዊና መንፈሳዊ መብቱንም በፈቃዱ ትቶ አል:: *እመልስ ዘንድ*፤ ክርስቶስን እንዲከተሉ ነው::

9፥20 *ከሕግ በታች ያሉትን*፤ በብሉይ ኪዳን ሕግና ሥርዐት ሥር ያሉትን አይሁድ ነው:: *ከሕግ በታች እንዳሉት ሆንሁ፤* ጳውሎስ ለአይሁድ ሲል ለእነርሱ ሕግ ራሱን አስገዛ (ሐሥ 16፥3፤ 18፥18፤ 21፥20-26)::

9፥21 *ለክርስቶስ ሕግ፤* የክርስቶስን ትምህርት ሳይሆን አይቀርም፤ ሆኖም ይህን ብቻ ያመለክታል ማለት አይደለም:: *ሕግ የሌላቸውን፤* በብሉይ ኪዳን ሕግ መሠረት ያልኖሩትን አሕዛብ ነው:: *ሕግ እንደሌለው ሰው ሆንሁ፤* ጳውሎስ ለክርስቶስ ያለውን ታማኝነት ሳያጓድል በአሕዛብ ሥርዐት ይመላለስ ነበር::

9፥22 *ደካሞች፤* ኅሊናቸው ደካማ የሆነባቸውን ነው (8፥9-12):: *ደካማ ሆንሁ፤* ጳውሎስ ባገኘው ነጻነት በመጠቀም ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ ለመብላት አልደፈረም (8፥9:13)::

9፥23 *በረከት፤* በረከቱ ወንጌልን በመስበክ ለክርስቶስ ታማኝ መሆኑ፣ በጌታ፣ "መልካም አደረግህ" መባሉና (ማቴ 25፥21) ሌሎች ወደ ክርስቶስ ሲመጡ ማየቱ ነበር::

9፥24 *በሩጫ ውድድር የሚሮጡ፤* የሩጫ ውድድር ለቆሮንቶስ ሰዎች አዲስ ነገር አልነበረም፤ ምክንያቱም ከኦሎምፒክ ውድድር፣ ቀጥሎ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ኢስታሚን በመባል የሚታወቅ ውድድር በየሁለት ዓመቱ ይደረግ ነበር:: *ሽልማቱን፤* በጥንት ዘመን ለአሸናፊዎች የሚሰጠው ሽልማት ውሎ አድሮ የሚረግፍ የአበባ ጉንጉን ነበር (ቊ 25)፤

9፥25 *ለዘላለም የማይጠፋውን አክሊል፤* 2ጢሞ 4፥8፤ ያዕ 1፥12፤ 1ጴጥ 5፥4፤ ራእ 2፥10፤ 3፥11፤ 4፥10 እና ማብ ይመ::

9፥26 *ግብ እንደሌለው ... አልሮጥም*፤ ፊል 3፥14 ይመ::

9፥27 *ሰውነቴን እየጎሰምሁ እንዲገዛልኝ አደርገዋለሁ፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የቦክስን ውድድር ከክርስቲያናዊ ሕይወት ጋር ያነጻጽራል:: እንዲያው ያለ ግብ ነፋስን መጎሰም ሳይሆን፣ ክርስቶስን ለማገልገል ሲል ሰውነቱን በሚገባ፣ ይቈጣጠራል:: *ውድቅ ሆኜ እንዳልቀር፤* ጳውሎስ ኀጢአትን እየተዋጋ በፍጹም ትጋት ጌታን ማገልገል እንዳለበት ተረድቶአል፤ አለበለዚያ አገልግሎቱ ከንቱ ይሆናል (1ቆሮ 3፥10-15 ይመ)::

10፥1 *ከደመናው በታች፤* በእግዚአብሔር ገዥነትና ምሪነት ሥር (ዘፀ 13፥21-22፤ ዘኍ 9፥15-23፤ 14፥14፤ ዘዳ 1፥33፤ መዝ 78፥14) ማለት ነው:: እርሱ እየመራቸው ሳለ የጐደለባቸው አንዳች ነገር አልነበረም፤ ባሕሩንም አሻገራቸው (ዘፀ 14፥22:29)::

*10፥2፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ እንደ *መሆናቸው መጠን*፣ በማዳን ዕቅዱ ውስጥ አንድነት አግኝተዋል፤ እግዚአብሔር ለሾመው መሪ፣ ለሙሴ ታዛዥ ሆነዋል (ዘፀ 14፥31):: *ተጠመቁ፤* የክርስቲያኖች ጥምቀት ክርስቶስ አዳኝና ጌታ መሆኑን አምነው መቀበላቸውን እንደሚያመለክት ሁሉ፣ የአይሁድም ጥምቀት ሙሴ ታዳጊያቸውና መሪያቸው መሆኑን አምነው መቀበላቸውን የሚያሳይ ነው::

10፥3-4 *መንፈሳዊ ምግብ ... መንፈሳዊ መጠጥ፤* መናውና ከዐለቱ የፈለቀው ውሃ፥ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ዘወትር እያዘጋጀ የሚያቀርበው ነገር ሁሉ ምሳሌ ነው (ዘፀ 16፥2-36፤ 17፥1-7፤ ዘኍ 20፥2-11፤21፥16)::

10፥4 *ያ፣ ዐለት ክርስቶስ ነበረ፤* ውሃው የፈለቀበት ዐለትና መናው፣ የሕይወት እንጀራና የሕይወት ውሃ በሆነው በክርስቶስ አማካይነት (ዮሐ 4፥14፤ 6፥30-35) ለምናገኘው ሰማያዊ መግቦት ምሳሌዎች ናቸው::

10፥5 *እግዚአብሔር በብዙዎቹ ደስ ስላልተሰኘ፤* እስራኤላውያን ታላቅ ዕድል ቢሰጣቸውም (ቊ 1-4)፣ እግዚአብሔርን አልታዘዙም፤ በዚህም ምክንያት እግዚአብሔር ፊቱን አዞረባቸው፤ ከግብፅ ከወጡት ጐልማሶች መካከል ወደ ከነዓን ለመግባት የተፈቀደላቸው ካሌብና ኢያሱ ብቻ ነበሩ (ዘኍ 14፥22-24፡ 28-35፤ ኢሱ 1፥1-2)::

10፥6 *እነርሱ ... እንደ ተመኙ፤* ጳውሎስ ለማለት የፈለ ገው በቊ 7-10 ላይ ተገልጾአል::

10፥7 *ጣዖት አምላኪዎች፤* ከወርቅ የተሠራውን የጥጃ ምስል በሚያመልኩበት ጊዜ የነበረውን ሁኔታ ያመለክታል (ዘፀ 32፥1-6)፤ ሕዝቡም ለጣዖት የተሠዋውን ምግብ በልቶ ነበርና (ከም 8 ጋር ያነጻጽሩ)::

*10፥8፤* የእስራኤል ሕዝብ ብዔልፌጎርን እንዳመለከ የሚያመለክት ሲሆን (ዘኍ 25፥1-9)፣ ይህን የሞዓባውያንን አምላክ ከሚያገለግሉ ወጣት ሴቶች ጋር ዝሙት ፈጽመው ነበር:: *ሀያ ሦስት ሺህ፤* በዕብራይስጡና በሰብዓ ሊቃናት ትርጕም በዘኍ

[9]ከእነርሱ አንዳንዶቹ ጌታን እንደ ተፈታተኑና በእባብ ተነድፈው እንደ ጠፉ፣ እኛም ጌታን አንፈታተን:: [10]ከእነርሱ አንዳንዶቹ እንዳጕረመረሙና በአጥፊው እንደ ጠፉ፣ አታጕረምርሙ::

[11]ይህ ሁሉ ምሳሌ ይሆን ዘንድ በእነርሱ ላይ ደረሰ፤ የዘመናት ፍጻሜ የደረሰብንን እኛን ለማስጠንቀቅም ተጻፈ:: [12]ስለዚህ ተደላድዬ ቆሜአለሁ የሚል ቢኖር እንዳይወድቅ ይጠንቀቅ:: [13]በሰዎች ሁሉ ላይ ከደረሰው የተለየ ፈተና አልደረሰባችሁም፤ እግዚአብሔር ታማኝ ነው፤ ስለዚህ ከምትችሉት በላይ እንድ ትፈተኑ አይተዋችሁም፤ ነገር ግን በምትፈተኑ በት ጊዜ ፈተናውን መታገሥ እንድትችሉ፣ መውጫ መንገዱን ያዘጋጅላችኋል::

## ከጣዖት ጋር አለመተባበር

[14]ስለዚህ ወዳጆቼ ሆይ፤ ከጣዖት አምልኮ ሽሹ:: [15]ይህን የምናገረው አስተዋይ ለሆኑ ሰዎች ነው፤ ስለምናገረው ነገር እናንተው ፍረዱ:: [16]የምንባርከው የበረከት ጽዋ ከክርስቶስ ደም ጋር ኅብረት ያለው አይደለምን? የምንቈርሰውስ እንጀራ ከክርስቶስ ሥጋ ጋር ኅብረት ያለው አይደለምን? [17]እንጀራው አንድ እንደ ሆነ፣ እኛም ብዙዎች ሆነን ሳለ አንድ አካል ነን፤ ሁላችን አንዱን እንጀራ እንካፈ ላለንና::

[18]እስቲ የእስራኤልን ሕዝብ አስቡ፤ መሥዋዕቱን የሚበሉት ከመሠዊያው ጋር ኅብረት አልነበራቸውምን? [19]ታዲያ፣ ለጣዖት የተሠዋ ነገርም ሆነ ጣዖቱ ራሱ ዋጋ ያለው ነገር ነው ማለቴ ነውን? [20]አይደለም፤ አሕዛብ የሚሠዉት ለእግዚአብሔር ሳይሆን ለአጋንንት ነው፤ ከአጋንንት ጋር እንድትተባበሩም አልሻም:: [21]የጌታን ጽዋና፣ የአጋንንትን ጽዋ በአንድ ላይ መጠጣት አትችሉም፤ ከጌታ ማዕድና ከአጋንንት ማዕድ ተካፋይ መሆን አትችሉም:: [22]ጌታን እናስቀናውን? በብርታትስ ከእርሱ እንበልጣለንን?

## የአማኞች ነጻነት

[23]"ሁሉ ነገር ተፈቅዶአል"፤ ነገር ግን ሁሉም ነገር አይጠቅምም፤ "ሁሉም ነገር ተፈቅዶአል"፤ ነገር ግን ሁሉም ነገር አያንጽም:: [24]እያንዳንዱ ሰው የባልንጀራውን ጥቅም እንጂ የራሱን ብቻ አይፈልግ::

[25]በኅሊና ምርምር ውስጥ ሳትገቡ በሥጋ ገበያ የሚሸጠውን ሁሉ ብሉ፤ [26]"ምድርና በውስጥዋ ያለው ሁሉ የጌታ ነውና::"

[27]የማያምን ሰው ጋብዞአችሁ ለመሄድ ብትፈልጉ በኅሊና ምርምር ውስጥ ሳትገቡ የቀረበላችሁን ሁሉ ብሉ:: [28]ነገር ግን አንዱ፣ "ይህ ለጣዖት የተሠዋ ነው" ቢላችሁ ይህን ስለ

10፥9 ዘፀ17፥2፤ ዘኍ21፥5፡6፤ መዝ78፥18፤95፥9፤ 106፥14
10፥10 ዘፀ12፥23፤ ዘኍ16፥41፡49፤17፥5፡ 10፤1ዜና21፥15፤ ዕብ11፥28
10፥11 ቍ6፤ ሮሜ4፥24፤13፥11
10፥12 ሮሜ11፥20፤ 2ቆሮ1፥24
10፥13 1ቆሮ1፥9፤ 2ጴጥ2፥9
10፥14 ቍ7፤ ዕብ6፥9፤1ጴጥ2፥11፤ 1ዮሐ2፥7፤5፥21፤ ይሁ3
10፥16 ማቴ14፥19፤ 26፥26-28፤ 1ቆሮ11፥23-25
10፥17 ሮሜ12፥5
10፥18 ዘሌ7፥6፡ 14፡15
10፥19 1ቆሮ8፥4
10፥20 ዘሌ17፥7፤ ዘዳ32፥17፤ መዝ106፥37፤ ራእ9፥20
10፥21 2ቆሮ6፥15፡16
10፥22 ዘዳ32፥16፡ 21፤1ነገ14፥22፤ መዝ78፥58፤ መክ6፥10፤ኢሳ45፥9፤ ኤር44፥8
10፥23 1ቆሮ6፥12
10፥24 ቍ33፤ ሮሜ15፥1፡2፤ 1ቆሮ13፥5፤ፊል2፥4፡21 10፥25 ሐሥ10፥15፤ 1ቆሮ8፥7 10፥26 ዘፀ9፥29፤19፥5፤ ኢዮ41፥11፤ መዝ24፥1፤50፥12፤ 1ጢሞ4፥4
10፥27 ሉቃ10፥7 10፥28 1ቆሮ8፥7፡ 10-12

25፥9 ላይ ሀያ አራት ሺህ ይላል፤ የጳውሎስ ትኵረት አኀዙ ላይ ሳይሆን፣ መልእክቱ ላይ ነው:: በሌላም በኩል ሊጠቀስ የፈለገው በአንድ ቀን ያለቁትን ብቻ እንጂ፣ በማግሥቱ ወይም ከዚያ በኋላ ያለቁትን ሳይጨምር ሊሆን ይችላል (ዘኍ 25፥4 ይመ)::

10፥10 *አታጕረምርሙ!* በዘኍ 16፥41 ላይ እንደተገለ ጸው ነው:: *በአጥፊው!* እዚህ ላይ ጳውሎስ እስራኤላውያን በሙሴና በአሮን ላይ ባጕረመረሙ ጊዜ (ዘኍ 16፥41)፣ ከእግዚ አብሔር ቍጣ መቅሠፍት ያመጣውን መልአክ (ዘኍ 16፥46-50) በዘፀ 12፥23 ላይ ከተጠቀሰው መልአክ ጋር ያገናዝበዋል::

10፥11 *የዘመናት ፍጻሜ!* ከጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ ጀምሮ እስከ ዳግም ምጽአቱና ከዚያም በኋላ ያለውን ዘመን ያጠቃልላል:: እግዚ አብሔር ባለፉት ዘመናት ለሕዝቡ ሲያደርግ የነበረው ሁሉ፣ በመሲሑ አማካይነት ፍሬያማ የሚሆንበት የመጨረሻው ዘመን ነው:: *ለማስጠንቀቅም ተጻፈ!* የሮሜ 15፥4 ማብ ይመ::

10፥13 *ፈተና!* መፈተን በራሱ ኀጢአት አይደለም፤ ጌታም ተፈትኖ ነበር (ማቴ 4፥1-11)፤ ለፈተና እጅ መስጠት ግን ኀጢአት ነው:: *መታገሥ እንድትችሉ!* በእግዚአብሔር ጸጋ የኀጢአትን ፈተና መቋቋም ይቻላል::

10፥14 *ከጣዖት አምልኮ ሽሹ!* በዘፀ 32፥1-6 ላይ ከተጠቀሰው ዐይነት ነው:: የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች ወደ እምነት የመጡት ከጣዖት አምላኪ ኅብረተ ሰብ ነው:: የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች የዕለት ተለት ተግባ ራቸውን በሚያከናውኑበት ጊዜ እንደ አፖሎ፣ አስክሌጲስ፣ ዲሜ ጥሪ፣ አፍሮዲቴና በሌሎች ተባዕትና እንስት አማልክት ስም የቆሙ አብያተ ጣዖታት ይጐበኙ ነበር:: በተለይ አፍሮዲቴ በተባለች እንስት አምላክ ስም በቆመው ቤተ ጣዖት ውስጥ፣ በርካታ ሴት አመንዝሮች ለዚሁ ተግባር ይገኙ ስለ ነበር የሚያጋጥመው ፈተና ብርቱ ነበር::

10፥16 *የበረከት ጽዋ!* በአይሁድ የፋሲካ በዓል ላይ ከሚጠ ጡት ጽዋዎች መካከል አንዱ ሲሆን፣ የጌታ እራት ሥርዐት የተመ ሠረተው በዚያው ወቅት ነበር (ማቴ 26፥17-30፤ ማር 14፥12-26፤ ሉቃ 22፥7-23):: *ከክርስቶስ ደም ጋር ኅብረት ያለው!* ከተሰቀለው ክርስቶስ ጋር ኅብረት ያለው መሆኑን የሚገልጽ መታሰቢያ ምልክት እንጂ በእርግጥ ደሙን መጠጣት አይደለም:: የጌታ እራት ሥርዐት ሆኖ በተመሠረተ ጊዜ፣ ጌታ ኢየሱስ ገና ደሙን አላፈሰሰም ነበር፤ ስለዚህ የጌታ እራት የሚያስታውሰን ጌታን ራሱን ነው (11፥25)::

10፥17 *አንዱን እንጀራ!* ብዙ አማኞች ከአንዱ እንጀራ መካፈላቸው የሚያሳየው የክርስቶስ አካል የሆነችውን የቤተ ክርስ ቲያንን አንድነት ነው፤ የምትመገበውም ያንኑ አንዱን የሕይወት እንጀራ ነው (ዮሐ 6፥33-58 ይመ)::

10፥18 *መሥዋዕቱን የሚበሉት ከመሠዊያው ጋር ኅብረት አልነበራቸውምን?* እስራኤላውያን በመሠዊያው ላይ ከቀረበው መሥዋዕት በበሉ ጊዜ (ዘሌ 7፥15፤ 8፥31፤ ዘዳ 12፥17-18)፣ ያመልኩ የነበረው የመሥዋዕቱን ሥርዐት የደነገገውንና መ ሠዊያው ራሱ የእርሱ የሆነውን እግዚአብሔርን ነው:: እንዲሁም አረማውያን መሥዋዕት በሚያቀርቡበት ጊዜ፣ ያመልኩ የነበረው አጋንንትን ነው (ቍ 20-21):: ደግሞም እንደ አምላክ ለሚቈጠር ጣዖታት የሚቀርበው መሥዋዕት ከንቱ እንደ ሆነ ተናግሮአል፤ ምክንያቱም ጣዖታቱ ራሳቸው ከንቱ ከመሆናቸውም በላይ፣ የሚመለኩት አማልክት በእርግጥ አምላክ አይደሉም:: እንደ እውነቱ ግን የሚመለኩት በእጅ የተሠሩት ጣዖታት ሳይሆኑ፣ በውስጣቸው ያደሩት አጋንንት ናቸው:: የእግዚአብሔር ሕዝብ ለጣዖታት የተሠዋ ሥጋ ከበሉ፣ ከጣዖት አምላኪዎች ጋር በቤተ ጣዖት መሳተፍ የለባቸውም፤ በቤተ ጣዖት ገብቶ መብላት ከአጋንንት ጋር እንደ መተባበር ይቈጠራል (ቍ 20)::

10፥22 *ጌታን እናስቀናውን?* ከአረማውያን ጋር የእነርሱን አማልክት በማምለክ ነው (ከዘፀ 20፥5፤ ዘዳ 32፥21፤ መዝ 78፥58 ጋር ያነጻጽሩ)::

10፥23 *ሁሉም ነገር አያንጽም!* የ6፥12 ማብ ይመ:: የራ ስን ነጻነትና መብት ማየት ብቻ ሳይሆን ለሌሎችም ማሰብ ያስፈልጋል (ቍ 24 ይመ፤ ከ 8፥1፤ ገላ 6፥2 ጋር ያነጻጽሩ)::

10፥25 *በሥጋ ገበያ የሚሸጠውን ሁሉ ብሉ!* ለጣዖት የተ ሠዋ ሥጋ ቢሆንም፣ ለገበያ በመቅረቡ ከአረማውያን ባዕድ አምልኮ አሠራር ነጻ ነው::

*10፥26!* ከመዝ 24፥1 የተወሰደ ሲሆን አይሁድ በማዕድ ላይ የሚጠቀሙበት የቡራኬ ቃል ነው (ከመዝ 50፥12፤89፥11 ጋር ያነጻጽሩ)::

10፥27 *የቀረበላችሁን ሁሉ ብሉ!* ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ ይሁን ወይም አይሁን አንዳች ጥያቄ አታቅርቡ፤ ሥጋው ለጣዖት የተ ሠዋ ቢሆንም ርእስ ጕዳዩ እስካልተነሣ ድረስ መብላት ይቻላል::

10፥28 *ስለ ነገራችሁ ሰው!* ሥጋው ለጣዖት የተሠዋ መሆኑን ዐውቃችሁ ብትበሉ፣ እንዲህ ስታደርጉ ያያችሁ ሰው (አማኝ ይሁን ወይም አይሁን) ነገሩን እንደ ደገፋችሁ፣ አልፎ

ነገራችሁ ሰውና ለኀሊናችሁ ስትሉ አትብሉ[*]:: [29]ይህን የምለውም ስለዚያ ሰው ኀሊና እንጂ ስለ አንተ አይደለም፤ ነጻነቴስ በሌላ ሰው ኀሊና ለምን ይመዘን? [30]ምግቡን በምስጋና የምበላ ከሆነ፣ ስግዚስብሔርን ባመሰገንሁበት ነገር ለምን እወቀሳለሁ?

[31]እንግዲህ ስትበሉም ሆነ ስትጠጡ፣ ወይም ማንኛውንም ነገር ስታደርጉ ሁሉንም ነገር ስስግዚስብሔር ክብር አድርጉት:: [32]ለአይሁድም ሆነ ለግሪኮች ወይም ስስግዚስብሔር ቤተ ክርስቲያን መሰናክል አትሁኑ፤ [33]እኔ ሰውን ሁሉ በማንኛውም ረገድ ለማስደሰት እንደ ምጥር እናንተም እንዲሁ አድርጉ፤ ብዙዎችም ይድኑ ዘንድ፣ ለራሴ የሚጠቅመውን ሳይሆን ለእነርሱ የሚጠቅመውን እሻለሁና::

**11** እኔ የክርስቶስን ምሳሌ እንደምከተል እናንተም የእኔን ተከተሉ::

## ሥርዐት ያለው አምልኮ

[2]በሁሉም ነገር ስለምታስቡልኝና ከእኔ የተቀበላችሁትን ትምህርት[†] አጥብቃችሁ ስለ ያዛችሁ አመሰግናችኋለሁ::

10፥29 1ቆሮ9፥1፡19
10፥30 ሮሜ14፥6
10፥31 ዘካ14፥21፤ ቈላ3፥17፤1ጴጥ4፥11
10፥32 ማቴ5፥29፤ ሐሥ20፥28፤24፥16፤ 1ቆሮ1፥2፤11፥16፡22፤ 15፥9፤2ቆሮ6፥3፤ 1ጢሞ3፥5፡15
10፥33 ቍ 24፤ ሮሜ11፥14፤15፥2፤ 1ቆሮ9፥22
11፥1 ሮሜ15፥3፤ 1ቆሮ4፥16፤1ጴጥ2፥21
11፥2 ቍ 17፡22፡ 23፤1ቆሮ4፥17፤ 15፥2፡3፤2ተሰ2፥15፤ 3፥6
11፥3 ዘፍ3፥16፤ 1ቆሮ3፥23፤ኤፌ1፥22፤ 5፥23
11፥4 ሐሥ11፥27
11፥5 ዘዳ21፥12፤ ሐሥ21፥9
11፥7 ዘፍ1፥26፤ 5፥1፤9፥6፤ያዕ3፥9

[3]ነገር ግን ይህን እንድታውቁ እወዳለሁ፤ የወንድ ሁሉ ራስ ክርስቶስ ነው፤ የሴትም ራስ ወንድ ነው፤ የክርስቶስም ራስ ስግዚስብሔር ነው:: [4]ራሱን ተከናንቦ የሚጸልይ ወይም ትንቢት የሚናገር ማንኛውም ወንድ የእርሱን ራስ ያዋርዳል፤ [5]ራሷን ሳትሸፍን የምትጸልይ ወይም ትንቢት የምትናገር ማንኛዋም ሴት የእርሷን ራስ ታዋርዳለች፤ ጠጕርዋን እንደ ተላጨች ይቈጠራልና:: [6]ሴት ራሷን የማትሸፍን ከሆነ፣ ጠጕርዋን ትቈረጥ፤ ጠጕሯን መቈረጥ ወይም መላጨት የሚያሳፍር መስሎ ከታያት ግን ራስዋን ትሸፈን:: [7]ወንድ ራሱን መከናነብ የለበትም፤[‡] ወንድ የስግዚስብሔር ምሳሌና ክብር ነውና፤ ሴት ግን የወንድ

[*]28 አንዳንድ ቅጆች *አትብሉ፤* "ምድርና በውስጧ ያለው ሁሉ የጌታ ናትና::"
[†]2 ወይም *ወግ*
[‡]4-7 ወይም የራሱን ጠጕር አስረዝሞ የሚጸልይ ወይም ትንቢት የሚናገር ማንኛውም ወንድ ራሱ የሆነውን ያዋርዳል፤ [5]ራሷን ሳትከናነብ የምትጸልይ ወይም ትንቢት የምትናገር ማንኛዋም ሴት ራሷ የሆነውን ታዋርዳለች፤ ጠጕራቸውን ከተላጩ ሴቶች አንዷ ትመስላለችና:: ሴት ራሷን የማትከናነብ ከሆነ፣ ጠጓሯን ታሳጥር፤ ጠጕሯን መቈረጥ ወይም መላጨት የሚያሳፍር ስለሆነ ግን እንደገና ታሳድገው:: [7]ወንድ ጠጕሩን ማስረዘም የለበትም፤

ተርፎም ጣዖት እንዳመለካችሁ ሊመስለው ይችላል:: *ለኀሊናችሁ ስትሉ፤* ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ መሆኑ በግልጽ ታውቆ ሳለ ይህን ሥጋ በመብላታችን፣ "የሌላውን ሰው ኀሊና" እንጐዳ ይሆናል (ቍ 29)፤ ከዚህ የተነሣ እንዲህ ያለውን ሥጋ መብላት ትክክል እንዳልሆነ ጥርጣሬ ቢኖረውም፣ ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ መብላት ምንም አይደለም እንዲል ያደርበዋል፤ ወይም ደግሞ ሰውየው አማኝ ካልሆነ፣ ክርስቲያኖች የሚያመለኩት እግዚአብሔርንና ጣዖትን አጣምረው ነው የሚል ግምት ያድርበታል::

10፥29 *ነጻነቴስ፤* ከሮሜ 14፥16 ጋር ያነጻጽሩ:: አንድ ክርስቲያን ባለው ነጻነት አንድ ነገር ከማድረጉ በፊት፣ ይህ ነገር ለእግዚአብሔር ክብር ይሆናል ወይ? የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን ያንጻል ወይ? የማያምኑ ሰዎች ክርስቶስን አዳኝና ጌታ አድርገው እንዲቀበሉ ያደርጋል ወይ? ብሎ ራሱን መጠየቅ አለበት (ቍ 31-33)::

10፥30 *እግዚአብሔርን ባመሰገንሁበት ነገር፤* ጳውሎስ ለጣዖት ስለ ተሠዋ ሥጋ ምስጋና ማቅረብ ይችላል፤ ምክንያቱም ጣዖት ከንቱ ነው፤ ለጣዖት የተሠዋውም ሥጋ እግዚአብሔር ከፈጠራቸው ነገሮች አንዱ ነው::

10፥31 *ሁሉንም ነገር ለእግዚአብሔር ክብር፤* በም 8-10 ባለው ክፍል የተነሣውን ሐሳብ አጠቃሎ የያዘው፣ በምናደርገው ነገር ሁሉ እግዚአብሔር መከበር አለበት የሚለው መርህ ነው::

10፥32 *መሰናክል አትሁኑ፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ የማሰናከያ ምክንያት አድርጎ የቈጠረው በተለይ ለጣዖት የተሠዋውን ሥጋ መብላት ነው (8፥13):: ለእግዚአብሔር ክብር መኖር፣ ለሰው ሁሉ (ለሚያምኑም ለማያምኑም) መልካም እንድናደርግ ግድ ይለናል::

10፥33 *ሰውን ሁሉ በማንኛውም ረገድ ለማስደሰት፤* ጳውሎስ እንዲህ ሲል ሰዎችን ሁሉ ለማስደሰት፣ ከወንጌል እውነት ነቅነቅ ይላል ማለት አይደለም፤ ይሁን እንጂ በዕለት ተዕለት አካሄዱ ሰዎች ኀሊናቸው እንዳይጐዳና ወንጌልን ከመቀበል ወደ ኋላ እንዳያፈገፍጉ ስለ ሰዎች ያስባል:: *ይድኑ ዘንድ፤* 9፥22 ይመ::

*11፥1፤* ቅደም ተከተሉን ያስተውሏል፤ (1) ትልቁ ምሳሌ ክርስቶስ ነው (ከ1ጴጥ 2፥21 ጋር ያነጻጽሩ)፤ (2) የክርስቶስ ሐዋርያት የእርሱን ምሳሌ ይከተላል ("እኔ እንደምከተል")፤ (3) እኛም የሐዋርያውን ምሳሌ መከተል ይገባናል::

*11፥3-16፤* በዚህ ክፍል የቀረበው ሐሳብ፣ በአምልኮ ጊዜ መታየት ስለሚገባው ሥርዐት እንጂ፣ በጥቅሉ ስለ ወንድና ሴት የእርስ በርስ ግንኙነት አይደለም:: ይሁን እንጂ ጳውሎስ በባልና በሚስት መካከል መኖር የሚገባው የእርስ በርስ ግንኙነት በአምልኮም ስፍራ መታየት እንዳለበት ይናገራል:: ቀደም ባለው ክፍል እንደ ገለጸው፣ ሁሉም ነገር ለእግዚአብሔር ክብር እንዲደረግ ምኞቱ ነው (10፥31)::

*11፥3* ራስ ለሰው አካል የክብር ምልክት እንደ መሆኑ፣ አንዳንዶች "ራስ" ሲባል የሚረዱት "ክብር" በሚለው ፅንሰ ሐሳብ ነው (ከቍ 4-5 ጋር ያነጻጽሩ):: በመሆኑም ክርስቶስ እግዚአብሔርን እንዳከበረ ሁሉ፣ ወንድ ክርስቶስን ማክበር፣ ሴትም ባሏን ማክበር ይገባቸዋል:: ሌሎች ደግሞ፣ "ራስ" የሚለውን የሚረዱት፣ "ሥልጣን" በሚለው ፅንሰ ሐሳብ ነው፤ (ይህም "ክብር" የሚለውን ፍሬ ሐሳብ ያጠቃልላል):: ደግሞም ጳውሎስ በኤፌ 1፥21-22 ("ከእግሩ በታች" "ከሁሉ በላይ ራስ"፣ ኤፌ 5፥22-23 ስለ መገዛት በሚናገረው ዐውደ ንባብ ውስጥ "ራስ" ስለ መሆን)እንዲሁም በቈላ 1፥18፡ 2፥10 ላይ ይህን ቃል በግልጽ የተጠቀመበት ሥልጣንን በሚያመለክት መልኩ ነው ይላሉ:: ስለዚህ ክርስቶስ በወንድ ላይ ሥልጣን እንዳለውና በወንድ መከበር እንዳለበት፣ ባልም በሚስቱ ላይ ሥልጣን ስላለው በሚስቱ መከበር ይኖርበታል::

*11፥4፤* በዚህ ቍጥር ላይ በመጀመሪያ የምናገኘው፣ "ራስ" የሚለው ቃል የሚያመለክተው የሰውን ጭንቅላት ወይም የራስ ቅል ነው፤ ቀጥሎ የምናገኘው፣ "ራስ" የሚለው ቃል ግን የሚያመለክተው የወንድ የበላይ ባለሥልጣን የሆነው ክርስቶስ ነው፤ ወይም ቃሉ ሁለቱንም ትርጕም ሊይዝ ይችላል:: በጳውሎስ ዘመን በነበረው ባሕል መሠረት፣ ወንዶች በአምልኮ ጊዜ ለአምላካቸው ያላቸውን አክብሮትና ተገዢነት ለመግለጽ ራሳቸውን አይከናነቡም ነበር:: አንድ ሰው ሲጸልይም ሆነ ትንቢት ሲናገር ራሱን ቢሸፍን፣ ለክርስቶስ የሚገባውን ክብር አልሰጠም ማለት ነው::

*11፥5-6፤* አንዲት ሴት የጠጕር መሸፈኛዋን ብታወልቅና ጠጕሯ በአደባባይ እንዲታይ ብታደርግ፣ ከሥነ ምግባር ውጭ እንደ ሆነችና ለዝሙት እንደምትጋብዝ ይቈጠር ነበር:: ሴት ራሷን የማትሸፍን ከሆነ፣ ጠጕሯን የተቈረጠች ወይም የተላጨች ያህል እንደ ሆነ ጳውሎስ ይናገራል:: ጠጕሯን የተላጨች ሴት አንድም የማስነወር ተግባር ፈጽማ በአደባባይ መዋረዷን አለበለዚያም ለባሏ የማትገዛ ጋጠ ወጥ መሆንዋን ያመለክታል:: ጳውሎስ ለእንደዚህ ዐይነት ሴቶች ያለው መልእክት፣ ሴት በአምልኮ ጊዜ ራሷን በመሸፈን ለባሏ ያላትን አክብሮትና ታዛዥነት ማሳየት አለባት የሚል ነው::

አንዳንዶች ሰዎች ጳውሎስ ጠጕርን ስለ መሸፈን አለመሸፈን ሲናገር በወቅቱ የነበረውን ባሕል እንደሚያወሳ አያስተውሉም:: ጳውሎስ የሥነ ፍጥረት ሥርዐትን በመጥቀሱ (ቍ 7-9)፣ እዚህ ላይ የሰጠው መመሪያ በእርሱ ዘመን ብቻ የሚወሰን አይደለም ይላሉ:: ስለዚህ በየትኛውም ዘመን የሚገኙት ሴቶች ጠጕራቸውን መሸፈን አለባቸው ይላሉ::

ሌሎች ደግሞ በዚህ ክፍል ስለ ሴቶች የተነሣው ሐሳብ ቋሚ መርህ ነው ይላሉ:: ይኸውም ሴቶች በማንኛውም ረገድ ለባሎቻቸው ሥልጣን በመገዛት አክብሮት ማሳየት አለባቸው፤ ይህንም ባለባበስ ብቻ ሳይሆን እግዚአብሔርን በመፍራት ማድረግ እንዳለባቸው ይናገራሉ:: በመጀመሪያ የተፈጠረው ወንድ ስለ ሆነ በሚስቱ ላይ ሥልጣን ሊኖረው ይገባል (1ጢሞ 2፥11-14 ይመ):: ሴት ከወንድ አካል ተወስዳ የተሠራችው (ዘፍ

ክብር ናት፤ [8]ምክንያቱም ሴት ከወንድ ተገኘች እንጂ ወንድ ከሴት አልተገኘም። [9]ደግሞም ሴት ለወንድ ተፈጠረች እንጂ ወንድ ለሴት አልተፈጠረም። [10]በዚህ ምክንያት፣ በመላእክትም ምክንያት፣ ሴት በሥልጣን ሥር መሆንዋን የሚያሳይ ምልክት በራስዋ ላይ ታድርግ።

[11]በጌታ ዘንድ ግን ሴት ያለ ወንድ፣ ወንድም ያለ ሴት አይሆንም። [12]ሴት ከወንድ እንደ ተገኘች ሁሉ፣ ወንድም ከሴት ይወለዳልና፤ ነገር ግን የሁሉም መገኛ እግዚአብሔር ነው። [13]እስቲ እናንተ ፍረዱ፤ ሴት ራስዋን ሳትሸፍን ወደ እግዚአብሔር መጸለይ ይገባታልን? [14]ወንድ ጠጕሩን ቢያስረዝም ነውር እንደሚሆንበት ተፈጥሮ እንኳ አያስተምራችሁምን? [15]ሴት ግን ጠጕርዋን ብታስረዝም ክብርዋ አይደለምን? ረጅም ጠጕር የተሰጣት መጐናጸፊያ እንዲሆናት ነውና። [16]እንግዲህ ማንም በዚህ ጕዳይ ላይ መከራከር ቢፈልግ፣ እኛም ሆን የእግዚአብሔር አብያተ ክርስቲያናት ከዚህ የተለየ ልማድ የለንም።

## የጌታ እራት

11፥23-25 ተጓ - ምብ ማቴ 26፥26-28፤ ማር 14፥22-24፤ ሉቃ 22፥17-20

[17]ነገር ግን በምትሰበሰቡበት ጊዜ ለሚጐዳ እንጂ ለሚጠቅም ስላልሆነ፣ ይህን ትእዛዝ ስሰጥ እያመሰገንኋችሁ አይደለም። [18]ከሁሉ አስቀድሞ በቤተ ክርስቲያን በምትሰበሰቡበት ጊዜ በመካከላችሁ መለያየት እንዳለ ሰምቻለሁ፤ ይህም ሊሆን እንደሚችል በከፊል አምናለሁ፤ [19]ከእናንተ መካከል እውነተኞቹ ተለይተው ይታወቁ ዘንድ፣ ይህ መለያየት በመካከላችሁ መኖሩ ግድ ነው። [20]በምትሰበሰቡበት ጊዜ የምትበሉት የጌታን እራት አይደለም፤ [21]በምትበሉበት ጊዜ አንዱ ሌላውን ሳይጠብቅ ምግቡን ይበላልና፤ አንዱ እየተራበ ሌላው ይሰክራል። [22]ለመሆኑ የምትበሉበትና የምትጠጡበት ቤት የላችሁምን? ወይስ የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን በመናቅ፣ ምንም የሌላቸውን ታሳፍራላችሁን? እንግዲህ ምን ልበላችሁ? በዚህ ነገር ላመስግናችሁን? ፈጽሞ አላመሰግናችሁም።

[23]እኔ ከጌታ የተቀበልሁትን ለእናንተ አስተላልፌአለሁና፤ ጌታ ኢየሱስ አልፎ በተሰጠበት ሌሊት፣ እንጀራን አንሥቶ [24]ከባረከ በኋላ ቈርሶ፣ "ይህ ስለ እናንተ የሚሆን ሥጋዬ ነው፤ ለመታሰቢያዬም አድርጉት" አለ። [25]እንዲሁም ከእራት በኋላ ጽዋውን አንሥቶ፣ "ይህ ጽዋ በደሜ የሚሆን አዲስ ኪዳን ነው፤ ስለዚህ ከጽዋው በምትጠጡበት ጊዜ ይህን ለመታሰቢያዬ አድርጉት" አለ። [26]ይህን እንጀራ በምትበሉበት ጊዜ፣ ይህንም ጽዋ በምትጠጡበት ጊዜ ሁሉ ጌታ እስኪመጣ ድረስ ሞቱን ትናገራላችሁ።

11፥8 ዘፍ2፥21-23፤ 1ጢሞ2፥13
11፥9 ዘፍ2፥18
11፥12 ሮሜ11፥36
11፥16 1ቆሮ7፥17፤ 10፥32
11፥17 ቍ 2፡22
11፥18 1ቆሮ1፥10-12፤3፥3
11፥19 1ዮሐ2፥19
11፥21 2ጴጥ2፥13፤ ይሁ12
11፥22 ቍ 2፡17፤ ቆሮ10፥32፤ያዕ2፥6
11፥23 ቍ 2፤ ገላ1፥12
11፥24 1ቆሮ10፥16
11፥25 ሉቃ22፥20፤ 1ቆሮ10፥16
11፥26 1ቆሮ1፥7

2፥21-24) አጋዥና አጋር ትሆነው ዘንድ ነው (ዘፍ 2፥20)፤ ስለዚህ እርሱ ራሷ መሆኑን ተረድታ (ቍ 3)፣ ለእርሱ በመገዛት ልታከብረው ይገባል።

የተቀሩት ደግሞ ይህ ክፍል በየትኛውም ዘመን ለሚፈጸም ጋብቻ ቋሚ የሆነ ትእዛዝ ሳይሆን፣ በዚያ ወቅት በቆሮንቶስ የነበረውን የጋብቻ ግንኙነት የሚያሳይና በወቅቱ የነበሩት ሴቶች ጠጕራቸውን ለምን መሸፈን እንደ ነበረባቸው ያመለክታል (ቍ 10) ይላሉ። ነገሩን ለማንጻጸር በቍ 11-12 የሰፈረውን ሐሳብ በመጥቀስ ወንዶችና ሴቶች፣ "በጌታ" (ቍ 11፤ ገላ 3፥28፤ 1ጴጥ 3፥7 ይመ) አንድ በመሆናቸው ተደጋግፈው መኖር እንዳለባቸው ያመለክታል ይላሉ።

11፥10 *በመላእክትም*፤ መላእክት እዚህ ላይ የተጠቀሱት፣ ክርስቲያኖች ባገኙት ሁለንተናዊ ድነት ደስ ስለሚሰኙና በአምልኮ ጊዜ ሊኖር የሚገባውን ሥርዐት በንቃት ስለሚከታተሉ ነው (ከኤፌ 3፥10፤ 1ጢሞ 5፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። *በሥልጣን ... ምልክት፤* አንዳንድ ሰዎች ይህ ሐረግ ሴት ከወንድ ጋር ፍጥረትን የመግዛት ሥልጣን እንዳላት ያሳያል ይላል (ዘፍ 1፥26-27)።

11፥13-14 *ይገባታልን? ... ተፈጥሮ እንኳ፤* ክርስቲያኖች በሚኖሩበት ኅብረተ ሰብ ውስጥ የአካሄዳቸውን ቅቡልነት ካሉበት ባህል አንጻር መመዘን ይገባቸዋል።

11፥16፤ ጳውሎስም ሆነ አብያተ ክርስቲያናት ወንዶች ጠጕራቸውን ማሳጠር ሴቶች ደግሞ ጠጕራቸውን ማስረዘም ይገባቸዋል የሚለውን የማኅበረ ሰቡን ልማድ ይከተሉ ነበር። በቍ 13-16 ላይ ያለውን ሐሳብ ሲሰነዝር መሠረት ያደረገው የተለመደውን የቤተ ክርስቲያን ወግ ነው።

11፥17 *እያመሰገንኋችሁ አይደለም፤* ከቍ 2 ጋር ያነጻጽሩ።

11፥18 *መለያየት፤* ጳውሎስ ከዚህ ቀደም በመካከላቸው ተነሥቶ ስለ ነበረው መከፋፈል መልስ ሰጥቶአል (1፥10-17)።

11፥19 እውነተኞቹ ... ይታወቁ ዘንድ፤ መለያየት አስከፊ ቢሆንም፣ በጎ ጐን አለው፤ ምክንያቱም በእግዚአብሔር ፊት ማን ታማኝና እውነተኛ እንደ ሆነ ለመለየት ይረዳል።

11፥20 *የምትበሉት የጌታን እራት አይደለም፤* የቆሮንቶስ ሰዎች የተሰበሰቡት የጌታን እራት ለመብላት ቢሆንም፣ እነርሱ ግን በሆዳምነታቸውና በአድልዎነታቸው አረከሱት።

11፥21 *አንዱ እየተራበ ሌላው ይሰክራል፤* የጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ከጌታ እራት ጋር በማያያዝ የምታዘጋጀው፣ "የፍቅር ግብዣ" የሚባል እራት (ከ2ጴጥ 2፥13፤ ይሁ 12 ጋር ያነጻጽሩ)። አንዳንዱ ሰው በየቤቱ አዘጋጅቶ ያመጣውን ምግብ በኅብረት የሚበሉበት ግብዣ ሳይሆን አይቀርም። በግሪኮች ልማድ መሠረት እያንዳንዱ ሰው በኅብረት የሚበሉትን ምግብ ከቤቱ ይዞ ይመጣል፤ ሀብታሞች ብዙ ምግብ ሲያመጡ ድኾች ግን አነስተኛ ምግብ ያመጡ ነበር፤ ሀብታሞች ከብጤዎቻቸው ጋር ወግነው እስኪጠግቡ ሲበሉ ድኾች ግን እንደተራቡ ይሄዳሉ።

11፥22 *በዚህ ነገር ላመስግናችሁን?* ቍ 17 ይመ።

*11፥23-26፤* ጳውሎስ በዚህ ክፍል የተናገረውን ከማቴ 26፥26-29፤ ማር 14፥22-25 በተለይም ከሉቃ 22፥17-20 ጋር ያለውን ተመሳሳይነት ያስተውሉ።

11፥23 *እኔ ከጌታ የተቀበልሁትን፤* ጳውሎስ እዚህ ላይ የሚናገረውን ሥርዐት በቀጥታ የተቀበለው ከጌታ ሊሆን ይችላል (ገላ 1፥11-17)፤ ወይም ደግሞ ይህን ሥርዐት ከጌታ ተቀብያለሁ ሲል በቀጥታ ከጌታ ሳይሆን በተዘዋዋሪ ከሌሎች ሳይሆን አይቀርም።

11፥24 *ከባረከ በኋላ፤* ምግብ ሲቀርብ ማመስገን የአይሁድ ልማድ ነው። *ሥጋዬ፤* የተቈረሰው እንጀራ ስለ ኀጢአተኞች የተሰጠው የጌታ ሥጋ ምሳሌ ነው (ሉቃ 22፥19)። *ለመታሰቢያዬም፤* የፋሲካ ምግብ ለመታሰቢያ እንደ ሆነ ሁሉ (ዘፀ 12፥14 ይመ)፣ የጌታም እራት ክርስቶስ ስለ ኀጢአተኞች መሞቱን የሚያስታውሰን ሥርዐት ነው።

11፥25 *ከእራት በኋላ፤* ከፋሲካ እራት በኋላ ነው። የጌታ እራት ሥርዐት የተጀመረው በጌታ ኢየሱስ ሲሆን፣ የተከበረውም ከፋሲካ እራት ጋር ተያይዞ ነበር (ከማቴ 26፥18-30፤ ከማርቆስና ከሉቃስ አቻ አገላለጽ ጋር ያነጻጽሩ)። *ጽዋውን፤* በጌታ ኢየሱስ ደም የቆመው የአዲሱ ኪዳን ምሳሌ ነው (ሉቃ 22፥20 ይመ፤ ከኤር 31፥31-34 ጋር ያነጻጽሩ)። (አሮጌው ኪዳን የሙሴ ወይም የሲና ኪዳን ነው ዘፀ 24፥3-8 ይመ)። በዚህ ኪዳን ምልክት አማካይነት በኢየሱስ ደም የተከፈለውንና የታተመውን የሕዝቡን ድነት እግዚአብሔር መቀበሉን ያረጋግጣል።

11፥26 *በምትበሉበት ጊዜ ... በምትጠጡበት ጊዜ፤* የጌታ እራት ሥርዐት በተወሰነ ጊዜ በቋሚነት መፈጸም ይኖርበታል፤ በየስንት ጊዜ መፈጸም እንዳለበት ግን ግልጽ መመሪያ አልተሰጠም። *እስከሚመጣ ድረስ፤* ከማቴ 26፥29 ጋር ያነጻጽሩ።

[27]እንግዲህ ማንም ሳይገባው፣ ይህን እንጀራ ቢበላ ወይም የጌታን ጽዋ ቢጠጣ፣ የጌታ ሥጋና ደም ባለ ዕዳ ይሆናል። [28]ማንም ሰው ከዚህ እንጀራ ከመብላቱና ከዚህ ጽዋ ከመጠጣቱ በፊት፣ ራሱን ይመርምር፤ [29]ምክንያቱም ማንም የጌታን ሥጋ ሳይገነዘብ* ቢበላና ቢጠጣ ፍርድ የሚያመጣበትን ይበላል፤ ይጠጣል። [30]ከእናንተ መካከል ብዙዎች የደከሙትና የታመሙት፣ አንዳንዶችም ያንቀላፉት በዚህ ምክንያት ነው። [31]ራሳችንን ብንመረምር ግን ባልተፈረደብን ነበር። [32]ነገር ግን ጌታ በሚፈርድብን ጊዜ እንገሠጻለን፤ ይኸውም ከዓለም ጋር አብረን እንዳንኰነን ነው።

[33]ስለዚህ፣ ወንድሞቼ ሆይ፤ ለመብላት በምትሰበሰቡበት ጊዜ እርስ በርሳችሁ ተጠባበቁ። [34]በምትሰበሰቡበት ጊዜ ለፍርድ እንዳይሆንባችሁ፣ ማንም የራበው ሰው ቢኖር በቤቱ ይብላ። ስለ ቀረው ነገር ደግሞ በምመጣበት ጊዜ እደነግጋለሁ።

## መንፈሳዊ ስጦታዎች

**12** ወንድሞች ሆይ፤ አሁን ደግሞ ስለ መንፈሳዊ ስጦታዎች ይህን እንድታውቁ እፈልጋለሁ። [2]አረማውያን በነበራችሁበት ጊዜ ወዲያና ወዲህ በመነዳት ድዳ ወደ ሆኑ ጣዖታት እንደ ተወሰዳችሁ ታውቃላችሁ። [3]ስለዚህ ማንም በእግዚአብሔር መንፈስ የሚናገር፣ "ኢየሱስ የተረገመ ነው" የሚል የለም፤ እንደዚሁም በመንፈስ ቅዱስ ካልሆነ በቀር፣ ማንም "ኢየሱስ ጌታ ነው" የሚል እንደሌለ እነግራችኋለሁ።

[4]ስጦታዎች ልዩ ልዩ ሲሆኑ፣ መንፈስ ግን አንድ ነው፤ [5]አገልግሎትም ልዩ ልዩ ሲሆን፣ ጌታ ግን አንድ ነው፤ [6]አሠራርም ልዩ ልዩ ሲሆን፣ ሁሉን በሁሉ የሚሠራው ግን ያው አንዱ እግዚአብሔር ነው።

[7]ነገር ግን መንፈስ ቅዱስን መግለጥ ለእያንዳንዱ ሰው የሚሰጠው ለጋራ ጥቅም ነው። [8]ለአንዱ በመንፈስ የጥበብን ቃል መናገር ይሰጠዋል፤ ለሌላው ደግሞ በዚያው መንፈስ የዕውቀትን ቃል መናገር ይሰጠዋል፤ [9]ለአንዱ በዚያው መንፈስ እምነት ይሰጠዋል፤ ለሌላው ደግሞ በዚያው በአንዱ መንፈስ የመፈወስ

11፥27 ዕብ10፥29
11፥28 2ቆሮ13፥5
11፥30 ማቴ9፥24
11፥31 መዝ32፥5፤ 1ዮሐ1፥9
11፥32 መዝ94፥2፤ 118፥18፤ምሳ3፥11፡ 12፤ዮሐ15፥18፡19፤ ዕብ12፥7-10፤ራእ3፥19
11፥34 ቍ21፡22፤ 1ቆሮ4፥19
12፥1 ሮሜ1፥11፤ 11፥25፤1ቆሮ1፥7፤ 14፥1፡37
12፥2 መዝ115፥5፤ ኤር10፥5፤ዕን2፤18፡ 19፤ኤፌ2፥2
12፥3 ዮሐ13፥ 13፤ሮሜ9፥3፤ 1ቆሮ16፥22፤1ዮሐ4፥ 2፡3
12፥4 ቍ8-11፤ ሮሜ12፥4-8፤ ኤፌ4፥11፤ዕብ 2፥4
12፥6 ኤፌ4፥6፤ ፊል2፥13
12፥7 1ቆሮ14፥12፤ ኤፌ4፥12
12፥8 1ቆሮ2፥6፤ 2ቆሮ8፥7 12፥9 ቍ28፡30፤ማቴ10፥1፤17፥19፡ 20፤1ቆሮ13፥2

* *ሳይለይ ወይም ሳይገነዘብ ማለት ነው።*

11፥27 *ሳይገባው፤* አንዳንድ የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች፣ "የፍቅር ግብዣ" በተባለው ሥርዐት ሲካፈሉ አክብሮት በጐደለውና ራስ ወዳድነት በተጠናወተው መንገድ ይካፈሉ እንደ ነበር የሚገልጽ ነው (ቍ 19-22)።

11፥28 *ራሱን ይመርመር፤* አንድ ሰው የልቡን ሐሳብና ተግባሩን እንዲሁም የጌታ እራት ስለሚያስተላፈው መልእክት ያለውን አመለካከት መመርመር አለበት። ይህም የጌታ እራት ከእግዚአብሔር ዘንድ መንፈሳዊ ጸጋ መቀበያ መንገድ ይሆንዋል።

11፥29 *የጌታን ሥጋ ሳይገነዘብ፤* "ሥጋ" የሚለው ቃል የጌታን አካል ወይም የክርስቶስ አካል የሆነችውን ቤተ ክርስቲያንን ያመለክታል (12፥13፡27 ይመ)። አንዱ አመለካከት ሰውየው የጌታን እራት በሚካፈልበት ጊዜ፣ የሚካፈለው ነገር የተሰቀለውን ክርስቶስ ሥጋ እንደሚወክል ሳይረዳ ይካፈላል የሚል ነው። ነገሩ እንዲህ ከሆነ ደሙ ለምን አልጠቀሰም የሚል ጥያቄ ያስነሣል፤ ሁለተኛው አመለካከት ደግሞ የጌታን እራት የሚካፈለው ሰው ቤተ ክርስቲያን የክርስቶስ አካል እንደሆነች ባለማስተዋል በቍ 20-21 ላይ የተጠቀሰው ራስ ወዳድነት ይታይበታል የሚል ነው። *ፍርድ፤* በማያምኑ ሰዎች ላይ የሚመጣውን ፍርድ ሳይሆን፣ በአማኞች ላይ የሚደርሰውን እንደ ሕመምና ሞት ያለውን የቅጣት ፍርድ ነው (ቍ 30)።

11፥30 *ያንቀላፉ፤* ሞትን ለመግለጽ በመጀመሪያው ምዕተ ዓመት የነበረ ዘይቤያዊ አነጋገር ነው።

11፥32 *እንገሠጻለን፤* አባት ልጁን እየቀጣ እንደሚያርም ሁሉ እኛም ድነት ያገኘን የእግዚአብሔር ልጆች እንቀጣለን፤ የምንቀጣውም በሠራነው ኀጢአት ንስሓ እንድንገባና (ከ2 ቆሮ 7፥10 ጋር ያነጻጽሩ) በጸጋ እንድናድግ ነው (2ጴጥ 3፥18፤ ዕብ 12፥7-11)።

11፥33 *ለመብላት በምትሰበሰቡበት ጊዜ፤* "የፍቅር ግብዣ" ኅብረትን የሚገልጽ ሌላው ሐረግ ነው (የቍ 21 ማብ ይመ)። እያንዳንዱ ሰው ለመብላት በሚቀርብበት ጊዜ ሌላውን መጠበቅ አለበት። አንድ በጣም የራበው ሰው ቢኖር፣ በቤቱ በልቶ መምጣት አለበት እንጂ፣ ራስ ወዳድነትንና አድልዎአዊነትን ይዞ ወደ ቤተ ክርስቲያን መምጣት የለበትም።

11፥34 *ስለ ቀረው ነገር ደግሞ በምመጣበት ጊዜ እደነግጋለሁ፤* የጌታን እራት በተመለከተ የእርሱን መልስ የሚሹ ሌሎች ችግሮች እንዳሉ ጳውሎስ ይጠቍማል፤ ይሁን እንጂ ለቀረው ነገር መልስ የሚሰጠው በሌላ ጊዜ ነው።

12፥1 *አሁን ደግሞ፤* ይህ ሐረግ ጳውሎስ የቆሮንቶስ ሰዎች በደብዳቤያቸው ላነሡት ተጨማሪ ጥያቄ መልስ መስጠቱን ይጠቍማል (ከ 7፥1፤ 8፥1፤ 16፥1 ጋር ያነጻጽሩ)። *መንፈሳዊ ስጦታዎች፤* ምንም እንኳ ከዚህ የተለየ የግሪክ ቃል ቢሆንም፣ የ1፥7 ማብ ይመ።

12፥2 *ድዳ ወደ ሆኑ ጣዖታት እንደ ተወሰዳችሁ፤* በአንድ ወቅት የቆሮንቶስ ሰዎች በተለያዩ ነገሮች ተገፋፍተው የማይናገሩ ጣዖታትን ያመልኩ ነበር (ከ 10፥19-20 ጋር ያነጻጽሩ)፤ አሁን ግን በመንፈስ ቅዱስ መመራት ይኖርባቸዋል።

12፥3 *"ኢየሱስ የተረገመ ነው" ... "ኢየሱስ ጌታ ነው"፤* ከመንፈስ ቅዱስ ዳግም የተወለደ ሰው ኢየሱስን መርገም አይችልም፤ ይልቁንም ከልቡ፣ "ኢየሱስ ጌታ ነው" ማለት የሚችል እርሱ ብቻ ነው (ከዮሐ 20፥28፤ እንዲሁም ከ1ዮሐ 4፥2-3 ጋር ያነጻጽሩ)። እዚህ ላይ፣ "ጌታ" ለሚለው የገባው የግሪኩ ቃል፣ ብሉይ ኪዳንን የተረጐሙት ሰብዓ ሊቃናት፣ "ያህዌ" ለሚለው የዕብራይስጡ ቃል የተጠቀሙበት ነው።

12፥4-6 *መንፈስ ግን አንድ ነው ... ጌታ ግን አንድ ነው ... አንዱ እግዚአብሔር ነው፤* እነዚህ ሐረጐች የሥላሴን አንድነት የሚያመለክቱ ሲሆን፣ የመንፈሳዊ ስጦታዎችን ልዩነትና አንድነት ያሳያሉ።

12፥4 *ስጦታዎች፤* መንፈስ ቅዱስ በውስጣችን ሲያድር የሚገለጡ የጸጋ ስጦታዎች ናቸው።

12፥5 *አገልግሎት፤* የግሪኩ ቃል በክርስቲያኑ ማኅበረ ሰብ ውስጥ የሚደረገውን ልዩ ልዩ አገልግሎት (ለምሳሌ ማዕድን ማገልገል፤ ሐሥ 6፥2-3)፤ ለመግለጽ ገብቶአል በኋላም ቃሉ በመጀመሪያው ምእተ ዓመት በነበረችው ቤተ ክርስቲያን የዲያቆናትን አገልግሎት ለማመልከት ገብቶአል (ፊል 1፥1)።

12፥6 *አሠራርም፤* የግሪኩ ቃል በሥራ ላይ ያለ (ሠሪና አድራጊ) ኀይልን ያመለክታል፤ የመንፈስ ቅዱስ ስጦታ በግልጽ የሚታይ ውጤት አለው።

12፥7 *መንፈስ ቅዱስን መግለጥ ለእያንዳንዱ ... የሚሰጠው ለጋራ ጥቅም ነው፤* እያንዳንዱ አማኝ መንፈሳዊ ስጦታ ተሰጥቶታል፤ ይህም መንፈስ ቅዱስ በአማኙ ሕይወት እንደሚሠራ ይመሰክራል። ስጦታዎች ሁሉ የተሰጡበት ዐላማ የክርስቲያኑን ማኅበረ ሰብ አባላት ለማነጽ (1ጴጥ 4፥10-11 ይመ)፤ በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ የነበሩ አንዳንድ ሰዎች ያደርጉ እንደነበረው ግን ለግል ጥቅም አይደለም።

12፥8 *ለአንዱ ... ለሌላው፤* አማኞች ሁሉ አንድ ዐይነት ስጦታ አይኖራቸውም፤ ደግሞም አንድ አማኝ ሁሉም ስጦታዎች አይኖሩትም። *የጥበብን ቃል ... የዕውቀትን ቃል፤* የክርስቲያኑ ማኅበረ ሰብ አንድ ውሳኔ ላይ ለመድረስ ወይም አንድን ተግባር ለመፈጸም መከተል የሚገባውን መንገድ ለመተለም ጥበብ ወይም ዕውቀት ባስፈለገ ጊዜ የሚያግዙ ስጦታዎች ናቸው።

12፥9 *እምነት፤* ለመዳን የሚያስፈልገው እምነት ሳይሆን፣ የክርስቶስ አካል በሆነችው ቤተ ክርስቲያን ውስጥ አንድን የተለየ ተግባር ለማከናወን የሚረዳ እምነት ነው። *የመፈወስ ስጦታዎች፤* የሁለቱ ቃላት መብዛት ልዩ ልዩ ዐይነት በሽታዎች እንዳሉና እግዚአብሔር እነዚህም በሽታዎች በተለያየ መንገድ እንደሚፈውስ ሳያሳይ አይቀርም።

ስጦታዎች ይሰጠዋል፤ [10]ለአንዱ ታምራትን የማድረግ፣ ለሌላው ትንቢትን የመናገር፣ ለሌላው ደግሞ መናፍስትን የመለየት፣ ለአንዱ በልዩ ልዩ ልሳን የመናገር፣ ለሌላው ደግሞ በልዩ ልዩ ልሳን[7] የተነገረውን የመተርጐም ስጦታ ይሰጠዋል። [11]እነዚህ ሁሉ የዚያው የአንዱ መንፈስ ስጦታዎች ሲሆኑ፣ ለእያንዳንዱ ሰው እርሱ ራሱ እንደ ፈቀደ ይሰጠዋል።

## አንድ አካል ብዙ ብልቶች

[12]አካል ብዙ ብልቶች ቢኖሩትም አንድ አካል ነው፤ ነገር ግን ብልቶች ብዙ ቢሆኑም አካል አንድ ነው። ክርስቶስም እንደዚሁ ነው። [13]አይሁድ ወይም የግሪክ ሰዎች ብንሆን፣ ባሪያ ወይም ነጻ ሰዎች ብንሆን፣ እኛ ሁላችን አንድ አካል እንድንሆን በአንድ መንፈስ ተጠምቀናልና፤ ሁላችንም አንዱን መንፈስ እንድንጠጣ ተሰጥቶናል።

[14]አካል የተሠራው ከብዙ ብልቶች እንጂ ከአንድ ብልት አይደለም። [15]እግር፣ "እኔ እጅ ስላልሆንሁ የአካል ክፍል አይደለሁም" ቢል ይህን በማለቱ የአካል ክፍል መሆኑ ይቀራልን? [16]ጆሮም፣ "እኔ ዐይን ስላልሆንሁ የአካል ክፍል አይደለሁም" ቢል ይህን በማለቱ የአካል ክፍል መሆኑ ይቀራልን? [17]አካል በሙሉ ዐይን ቢሆን ኖሮ፣ መስማት ከየት ይገኝ ነበር? አካል በሙሉ ጆሮ ቢሆን ኖሮ፣ ማሽተት ከየት ይገኝ ነበር? [18]ነገር ግን እግዚአብሔር እንደ ወደደ እያንዳንዱን በየቦታው መድቦ አል። [19]ሁሉም አንድ ብልት ቢሆን ኖሮ አካል ከየት ይገኝ ነበር? [20]እንግዲህ ብልቶች ብዙ ናቸው፣ አካል ግን አንድ ነው።

[21]ዐይን እጅን፣ "አታስፈልገኝም" ሊለው አይችልም፤ ራስም እግርን፣ "አታስፈልጉኝም" ሊለው አይችልም። [22]እንዲያውም ደካማ የሚመስሉት የአካል ብልቶች እጅግ አስፈላጊ ናቸው። [23]የተናቁ ለሚመስሉን ብልቶች ይበልጥ ክብር እንሰጣቸዋለን፤ ደግሞም የምናፍርባቸውን ብልቶች ይበልጥ እንንከባከባቸዋለን፤ [24]የማናፍርባቸው ብልቶቻችን ግን ይህ አያስፈልጋቸውም። እግዚአብሔር ግን የአካል ብልቶችን አንድ ላይ አገጣጥሞ ክብር ለሚጐድላቸው

12፥10 ቍ28-30፤ ማር16፥17፤ገላ3፥5፤ ኤፌ4፥11፤1ዮሐ4፥1
12፥11 ቍ4
12፥12 ቍ27፤ ሮሜ12፥5
12፥13 ዮሐ7፥37-39፤ገላ3፥28፤ ኤፌ2፥18፤ቈላ3፥11
12፥14 ቍ12:20
12፥18 ቍ11:28
12፥20 ቍ12:14፤ ሮሜ12፥5

[7]10 ወይም *ቋንቋ*፤ እንዲሁም ቍ28 ይመ

12፥10 *ታምራትን የማድረግ፤* ቃል በቃል ቢተረጐም "የማድረግ ኀይል" ማለት ነው። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ታምር በሰው አእምሮ ሊገለጽ የማይችል፣ ከተፈጥሮ ሕግ ውጭ የሆነ ነገር ነው፤ የሚደረገውም የእግዚአብሔርን ኀይልና ዐላማ ለመግለጽ ነው። *ትንቢትን፤* የእግዚአብሔር ሐሳብ በመንፈስ ቅዱስ አማካይነት ለአንድ አማኝ ሲገለጥ ነው፤ ይኸውም የወደፊቱን አስቀድሞ መናገር (አጋቦስ በሐሥ 11፥28፤ 21፥10-11 ላይ ከተናገረው ጋር ያነጻጽሩ)፤ ወይም በአንድ የተወሰነ ሁኔታ ውስጥ የእግዚአብሔርን ፈቃድ መግለጥ ሊሆን ይችላል (ከ14፥29-30፤ ከሐሥ 13፥1-2 ጋር ያነጻጽሩ)። *መናፍስትን የመለየት፤* ከክፉ መናፍስት ሊመጡ የሚችሉ ሐሰተኛ ትንቢቶች ስላሉ፣ እውነተኛውን ትንቢት ከሐሰተኛው ለመለየት ይህ ስጦታ አስፈላጊ ነው (ከ1ዮሐ 4፥1-6 ጋር ያነጻጽሩ) *በልዩ ልዩ ልሳን፤* አንዳንድ ሰዎች "ልሳን" ለሚለው የገባው የግሪኩ ቃል፣ "ቋንቋ" ወይም "የንግግር ዘዬ" ማለት በመሆኑ፣ ሐዋርያት በበዓለ አምሳ ቀን እንደ ተናገሩት ዐይነት (ሐሥ 2፥4:6:11 ይመ፤ ከ1ቆሮ 14፥9-10 ጋር ያነጻጽሩ) ከዚህ በፊት በማያውቁት ቋንቋ መናገር ነው ይላሉ። ሌሎች ደግሞ ከም 12-14 ባለው ክፍል ውስጥ፣ "ልሳን" የሚለው ቃል እጅግ ከመፈንደቅ የተነሣ ትርጒም በሌለው ቋንቋ ምስጋናንና ጸሎትን ማነብነብን ጨምሮ (13፥1፤ 14፥2:10) ምድራዊና ሰማያዊ ቋንቋን ያመለክታል ይላሉ። *በልዩ ልዩ ልሳን የተነገረውን የመተርጐም፤* አድማጮች የሚነገረውን ሰምተው እንዲታነጹ መልእክቱን እነርሱ በሚሰሙት ቋንቋ ማስተላለፍ ነው (ከ 14፥5: 13: 27-28 ጋር ያነጻጽሩ)።

12፥11 *እርሱ ራሱ እንደ ፈቀደ፤* እያንዳንዱ አማኝ ሊቀበል የሚገባውን ስጦታ ወይም ስጦታዎች የሚወስንና የሚያድል መንፈስ ቅዱስ ነው።

12፥12 *ብዙ ብልቶች ... አንድ አካል፤* ይህ ምሳሌ የአንዱ የክርስቶስ አካል ብልቶች የሆኑት የእግዚአብሔር ሰዎች የሚለማመዷቸውን መንፈሳዊ ስጦታዎች አንድነትና ልዩነት ያመለክታል። *ክርስቶስም፤* ክርስቶስ፣ ራሷ የሆነውንና እርሷም አካሉ የሆነችውን ቤተ ክርስቲያንን ነው (ኤፌ 1፥23-23)።

12፥13 *አይሁድ ወይም የግሪክ ሰዎች፤* በክርስቶስ የሆኑትን ዘርም ሆነ ባሕል አይለያቸውም። *ባሪያ ወይም ነጻ ሰዎች፤* የክርስቶስ በሆኑ ሰዎች መካከል፣ የወገንም ሆነ የመደብ ልዩነት የለም። *ሁላችን አንድ አካል እንድንሆን በአንድ መንፈስ ተጠምቀናል፤* መንፈሳዊ ጥምቀት መጠመቅ፣ በመንፈስ ቅዱስ ዳግም መወለድና (ዮሐ 3፥3:5)፤ ከክርስቶስ አካል ጋር አንድ መሆን ነው። *ሁላችንም አንዱን መንፈስ እንድንጠጣ ተሰጥቶናል፤* በሕዝቡ ሁሉ ልብ እንዲያድር፣ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስን ሰጥቶአል (6፥9)፤ ይህንንም ያደረገው ሕይወታቸው የመንፈስ ቅዱስን ፍሬ እንዲያፈራ ነው (ገላ 5፥22-23 ይመ፤ ከዮሐ 7፥37-39 ጋር ያነጻጽሩ)።

*12፥14-20፤* የተቀበሉት ስጦታ ዝቅተኛና ስፍራ የማይሰጠው መስሎ ለሚታያቸው ክርስቲያኖች የተነገረ ነው፤ ምክንያቱም ጐልተው የሚታዩ (በልሳን መናገርና የመሳሰሉት) ስጦታዎች በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ትልቅ ስፍራ ተሰጥቶአቸው ስለ ነበር፣ ይህን ስጦታ ያላገኙ ወገኖች የዝቅተኝነት ስሜት አድሮባቸው ነበር።

*12፥14፤* የሰው አካል በሚገባ ይሠራ ዘንድ የተለያዩ ብልቶች እንደሚያስፈልጉት ሁሉ፣ የክርስቶስ አካል ብልቶችም የተለዩ ስጦታዎች አሏቸው፤ የእያንዳንዱም ስጦታ ጥቅም፣ አንዱን የክርስቶስን ዐላማ እውን ማድረግ ነው። እያንዳንዱ ብልት (ምዕመን) መላውን አካል ለመጥቀም፣ ስጦታውን በሚገባ ተግባር ላይ ማዋል አለበት፤ ደግሞም በተቀመጠበት ስፍራ የተሰጠውን ኀላፊነት በሚገባ መወጣት ይገባዋል፤ ለምሳሌ የጥበብና የዕውቀት ቃል ስጦታ ያላቸው እንዲሁም ሐዋርያ፣ ሽማግሌና (1ጢሞ 5፥1) ዲያቆን (ሐሥ 6፥1-6) ለመሆን ሥልጣን የተሰጣቸውም ኀላፊነታቸውን በአግባቡ መወጣት አለባቸው።

*12፥18፤* ጳውሎስ በእግዚአብሔር ሉዓላዊ ፈቃድ፣ የሰው አካል የተለያዩ ብልቶች እንዲኖሩት የተደረገበትን ምክንያት ይናገራል፤ ይህንንም ምሳሌ በማድረግ እግዚአብሔር በክርስቶስ አካል ውስጥ አንድ ዐይነት ስጦታ ሳይሆን ልዩ ልዩ ስጦታዎች ያሏቸው የተለያዩ ክርስቲያኖች እንዳስቀመጠ ያወሳል፤ የተለያዩ ስጦታዎች እንዲኖሩ የተደረገውም አንዱን የእግዚአብሔር ዐላማ እውን ለማድረግ ነው። እግዚአብሔር አንድነትን ለማምጣት ልዩነትንም ይጠቀማል።

*12፥21-26፤* የተቀበሉት ስጦታ ከፍተኛ ስፍራ የሚሰጠው መስሎ ለሚታያቸው የተነገረ ነው። ከእነዚህ ቍጥሮች እንደምንረዳው፣ አንዳንድ ስጦታዎች (ለምሳሌ በልሳን መናገር) ከምንም በላይ ትልቅ ስጦታ ተደርገው ይታዩ ነበር።

*12፥21፤* በአንድ አካል ውስጥ የሚገኙ የተለያዩ ብልቶች እርስ በርስ የመደጋገፍ ባሕርይ እንዳላቸው ከዚህ መርሕ እንረዳለን፤ በክርስቶስ አካል ውስጥ የሚገኙት ክርስቲያኖችም፣ የተለያዩ ተግባራት በሚያከናውኑበት ጊዜ እርስ በርስ ተደጋጋፊ ናቸው።

12፥22 *ደካማ ... እጅግ አስፈላጊ ናቸው፤* በክርስቶስ አካል ውስጥ ዝቅተኛ ስፍራ ያላቸው የሚመስሉ ክርስቲያኖች፣ በእርግጥ ጠቃሚና አስፈላጊ ናቸው።

12፥23 *የተናቁ ለሚመስሉን ብልቶች ይበልጥ ክብር እንሰጣቸዋለን፤* እምብዛም ስፍራ ለሌላቸው የሰውነት ክፍሎች የተለየ እንክብካቤ እንደምናደርግ ሁሉ፣ ጐልቶ የማይታይ ስጦታ ያላቸውንም ክርስቲያኖች ማክበርና ማገዝ ይኖርብናል። *የምናፍርባቸውን ብልቶች ይበልጥ እንንከባከባቸዋለን፤* በቤተ ክርስቲያን ውስጥ አገልግሎታቸው በሰው ፊት ለማይታይ ክርስቲያኖች የተለየ አክብሮት መስጠት ይገባል።

*12፥24፤* በሰው ፊት ጐልቶ የሚታይ ስጦታ ላላቸው የተለየ ክብር መስጠት አያስፈልግም።

የበለጠ ክብር ሰጥቶአቸዋል፤ [25]ይህንም ያደረገው በአካል ብልቶች መካከል መለያየት ሳይኖር፣ እርስ በርሳቸው እኩል እንዲተሳሰቡ ነው። [26]አንድ ብልት ቢሠቃይ ብልቶች ሁሉ አብረው ይሠቃያሉ፤ አንድ ብልት ቢከበር ሌሎቹም ብልቶች አብረው ደስ ይላቸዋል።

[27]እንግዲህ እናንተም የክርስቶስ አካል ናችሁ፤ እያንዳንዳችሁም የአካሉ ብልቶች ናችሁ። [28]እግዚአብሔር በቤተ ክርስቲያን ውስጥ አንደኛ ሐዋርያትን፣ ሁለተኛ ነቢያትን፣ ሦስተኛ መምህራንን፣ ቀጥሎም ታምራት አድራጊዎችን፣ የመፈወስ ስጦታዎች ያላቸውን፣ ሌሎችን የመርዳት ስጦታ ያላቸውን፣ የማስተዳደር ስጦታ ያላቸውንና በልዩ ልዩ ልሳን የመናገር ስጦታ ያላቸውን ሰዎች መድቦአል። [29]ሁሉ ሐዋርያት ናቸውን? ሁሉስ ነቢያት ናቸውን? ሁሉስ መምህራን ናቸውን? ሁሉስ ታምራት ያደርጋሉን? [30]ሁሉስ የመፈወስ ስጦታዎች አላቸውን? ሁሉስ በልሳኖች ይናገራሉን[ሀ]? ሁሉስ ይተረጉማሉን? [31]ነገር ግን ከሁሉ የሚበልጠውን ስጦታ በብርቱ ፈልጉ።[ለ]

12፥27 ሮሜ12፥5፤ ኤፌ1፥23፤4፥12፤ ቈላ1፥18፡24
12፥28 ቍ9፡10፤ ማር16፥17፤ ሮሜ12፥6-8፤ 1ቆሮ10፥32፤ ኤፌ4፥11
12፥30 ቍ10
12፥31 1ቆሮ14፥1፡39
13፥1 ቍ8፤ ማር16፥17
13፥2 ቍ8፤ ማቴ17፥20፤21፥21፤ ሐሥ11፥27፤ 1ቆሮ12፥9፤14፥2፤ 2ቆሮ8፥7፤ኤፌ4፥11
13፥3 ዳን3፥28፤ ሉቃ19፥8፤ሐሥ2፥45
13፥4 1ቆሮ5፥2፤ 1ተሰ5፥14
13፥5 ኢዮ14፥16፡17፤ምሳ10፥12፤17፥9፤ማቴ5፥22፤ 1ቆሮ10፥24፤ 1ጴጥ4፥8

## ፍቅር

ደግሞም ከሁሉ የሚበልጠውን መንገድ አሳያችኋለሁ።

**13** በሰዎችና በመላእክት ልሳን[ሐ] ብናገር፣ ፍቅር ግን ከሌለኝ እንደሚጮኽ ናስ ወይም እንደሚንሿሿ ጸናጽል ነኝ። [2]የትንቢት ስጦታ ቢኖረኝ፣ ምስጢርን ሁሉና ዕውቀትን ሁሉ ባውቅ፣ ተራራንም ከቦታው የሚነቅል እምነት ቢኖረኝ፣ ፍቅር ግን ከሌለኝ ከንቱ ነኝ። [3]ያለኝን ሁሉ ለድኾች ብሰጥ፣ ሰውነቴም እንዲቃጠል ለእሳት ብዳርግ፣[መ] ፍቅር ግን ከሌለኝ ምንም አይጠቅመኝም።

[4]ፍቅር ታጋሽ ነው፤ ደግሞም ቸር ነው። ፍቅር አይመቀኝም፤ አይመካም፤ አይታበይም፤ [5]ተገቢ ያልሆነ ነገር አያደርግም፤ ራስ ወዳድ አይደለም፤ አይበሳጭም፣ በደልን አይ

[ሀ]30 ወይም፣ *በሌሎች ቋንቋዎች*
[ለ]31 ወይም፣ *እናንተ ግን ከሁሉ የሚበልጠውን ስጦታ በብርቱ እየፈለጋችሁ።*
[ሐ]1 ወይም *ቋንቋዎች*
[መ]3 አንዳንድ የጥንት ቅጆች፣ *እንድታበይ ሰውነቴንም አሳልፌ ብሰጥ ይላሉ*

12፥25 *መለያየት ሳይኖር፤* 1፥10-12 ይመ።

12፥26 *ብልቶች ሁሉ አብረው ይሠቃያሉ፤* ከክርስቶስ አካል አንዱ ብልት ቢሠቃይ፣ ሌሎች ክርስቲያኖችም የሥቃዩ ተካፋይ ይሆናሉ (በሐሥ 12፥1-5 ላይ ካለው ከያዕቆብ ሰማዕትነትና ከጴጥሮስን መታሰር ጋር ያነጻጽሩ)።

12፥27 *እናንተም የክርስቶስ አካል ናችሁ፤* በቆሮንቶስ ለነበረችው አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን የተነገረው ነው፤ ዓለም ዐቀፋዊቷ ቤተ ክርስቲያን የክርስቶስ አካል እንደ ሆነች ሁሉ፣ እያንዳንዷ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያንም የክርስቶስ አካል ናት።

*12፥28፤* እዚህ ላይ ያለው ዝርዝር በቍ 8-10 ላይ ከሚገኘው ዝርዝር ለየት ያለ ነው (ያንኑ ማብ ይመ)። እዚህ ላይ ጳውሎስ ከኤፌ 4፥11 ላይ ስጦታ ያላቸውን ሦስት አገልጋዮች፣ ከቍ 8-10 ላይ ደግሞ አምስት የመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎችን ይጠቅሳል። ሐዋርያትና ነቢያት የቤተ ክርስቲያን መሠረት የጣሉ ናቸው (ኤፌ 2፥20)፤ ማስተማር ደግሞ ከእረኛነት (መጋቢነት) ጋር የተያያዘ ነው (ኤፌ 4፥11፤ 1ጢሞ 3፥2)። እነዚህ ስጦታ ያላቸው ሦስት አገልጋዮች በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ካላቸው አገልግሎት ደረጃ አንጻር፣ "አንደኛ"፣ "ሁለተኛ"፣ "ሦስተኛ" ተብለዋል። ደግሞም የተለያዩ ስጦታዎች እንዳሉ ለማመልከት የተቀሩት ስጦታዎች፣ "ቀጥሎም" ከሚለው ማያያዣ በኋላ ተዘርዝረዋል። ጳውሎስ መንፈሳዊ ስጦታዎቹን የዘረዘረው ለናሙና ያህል ብቻ ይመስላል። ከቍጥር 28 የመጀመሪያው ክፍል ("አንደኛ"፣ "ሁለተኛ"፣ "ሦስተኛ") ከተባሉት በስተቀር ሌሎቹን ስጦታዎች በማበላለጥ ደረጃ አላስቀመጣቸውም፤ ምክንያቱም ቀደም ሲል ስጦታዎች ሁሉ እኩል ጠቃሚ መሆናቸውን በአጽንዖት ገልጾአል (ቍ 21፥26)። *ሐዋርያት፤* ጌታ ኢየሱስ በምድራዊ አገልግሎቱ ከእርሱ ጋር እንዲሆኑና ወጥተውም ወንጌልን እንዲሰብኩ የመረጣቸው (ማር 3፥14)፣ የትንሣኤው ምስክሮች ነበሩ (ሐሥ 1፥21-22)። አንዳንድ ጊዜ ቃሉ ሰፋ ያለ ትርጒም ሊይዝ ይችላል (ሮሜ 16፥7፤ ገላ 1፥19)። *ተአምራት ... የመፈወስ ... ልሳን፤* የቍ9-10 ማብ ይመ። *ሌሎችን የመርዳት፤* እዚህ ላይ ሐረጉ የሚያመለክተው ድኾችን፣ መጻተኞችን፣ ሕመምተኞችንና ኀዘንተኞችን መንከባከብ ቢሆንም (ከሐሥ 6፥1-6 ያነጻጽሩ)፣ ሌሎችን ለመርዳት የሚደረገው ማንኛውም ተግባር ከመንፈስ ቅዱስ ስጦታ የተነሣ ሊሆን ይችላል (ከሮሜ 12፥6-8 ጋር ያነጻጽሩ)። *የማስተዳደር፤* የማስተዳደር ስጦታ ያላቸው ሰዎች ቤተ ክርስቲያንን ለማደራጀት፣ ዕቅድ ለማውጣትና መንፈሳዊ መርሐ ግብር ለማዘጋጀት የሚችሉት በመንፈስ ቅዱስ ነው።

12፥29-30 *ሁሉ ሐዋርያት ናቸውን?* ክርስቲያኖች የተለያየ ስጦታ አላቸው፤ ስለዚህ ሁሉም ሰው አንድ ዐይነት ስጦታ መሻት የለበትም።

12፥31 *ከሁሉ የሚበልጠውን ስጦታ በብርቱ ፈልጉ፤* ቍ 28፤ 14፥1፡5፡12፡39 ይመ። ይህ ሐረግ በአማራጭ ትርጒሙ ላይ እንደ ተመለከተው፣ "እናንተ ግን ከሁሉ የሚበልጠውን ስጦታ በብርቱ እየፈለጋችሁ" ነው፤ የሚለው ትክክል ከሆነ የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች ለእነርሱ ትልቅ መስሎ በሚታያቸው ስጦታ አማካይነት የራሳቸውን ክብር ይፈልጉ ነበር። *ከሁሉ የሚበልጠውን መንገድ፤* ጳውሎስ መንፈሳዊ ስጦታዎችን ሁሉ እንዴት መለማመድ እንደሚገባ ትክክለኛውን መንገድ ይጠቁማል፤ ያም መንገድ የፍቅር መንገድ ነው። ጳውሎስ ፍቅር የጸጋ ስጦታ መሆኑን አይናገርም፤ ይልቁንም ፍቅር የመንፈስ ፍሬ ነው (ገላ 5፥22)።

13፥1-3 *ልሳን ... የትንቢት ... እምነት ... ብሰጥ፤* ጳውሎስ አራት ስጦታዎችን ለአብነት ያህል መርጦአል። በእነዚህ ስጦታዎች የሚያስደንቅ ነገር ማከናወን ቢቻልም እንኳ፣ ነገሩ በፍቅር እስካልተደረገ ድረስ ከንቱ ነው።

13፥1 *በሰዎችና በመላእክት ልሳን፤* ጳውሎስ ግነትን ተጠቅሞአል። ሰዎች የሚናገሩትን ቋንቋ ብቻ ሳይሆን መላእክትም የሚናገሩትን ቋንቋ መናገር ቢችል እንኳ፣ ፍቅር ከሌለው ባዶ ጩኸት እንደሆነ ይናገራል። *ፍቅር፤* የግሪኩ ቃል ለራስ ጥቅም ሳይሆን፣ ለሌሎች ማሰብን ያመለክታል፤ እንዲህ ዐይነት ፍቅር ያለው ሰው ለሌሎች መልካም ነገር የሚያደርገው በሰዎቹ መልካምነት ላይ ተመሥርቶ ሳይሆን፣ እግዚአብሔር ሌሎችን እንድንወድ የሰጠውን ትእዛዝ በማክበር ነው። ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ በመስቀል ላይ እንደ ገለጠው ዐይነት ፍቅር ማለት ነው (ከዮሐ 13፥34-35፤ 1ዮሐ 3፥ 16 ጋር ያነጻጽሩ)።

13፥2 *ምስጢርን ሁሉና ዕውቀትን ሁሉ፤* ጳውሎስ ሊኖረው የሚችለውን የመረዳት መጠን ለመግለጽ፣ አሁንም ግነትን ሲጠቀም እናያለን። አንድ ሰው ወሰን የሌለው ዕውቀት ቢሰጠው ነገር ግን ይህን ስጦታ በፍቅር ባይዝና ባይጠቀምበት ከንቱ ነው። *ተራራንም ከቦታው የሚነቅል እምነት፤* እግዚአብሔር በተለየ መንገድ የሚያስፈልገንን ነገር እንዲያዘጋጅልን በእርሱ የምንታመንበት ልዩ ችሎታ ነው። ጳውሎስ እዚህም ላይ ግነትን ተጠቅሞአል።

13፥3 *ሰውነቴም እንዲቃጠል ለእሳት ብዳርግ፤* ብዙ የጥንት ክርስቲያኖች በእሳት ተቃጥለው በሰማዕትነት ሕይወታቸው ያለፈበትን አሟሟት ያመለክታል። እጅግ ታላቅ መሥዋዕትነት ብንከፍል እንኳ፣ በፍቅር እስካልሆነ ድረስ ምንም ፋይዳ የለውም።

13፥4-7፤ እዚህ ላይ ፍቅር በአዎንታዊና በአሉታዊ መልክ ተገልጾአል።

13፥4 *አይታበይም፤* 8፥1ይመ።

13፥5 *ተገቢ ያልሆነ ነገር አያደርግም፤* በአምልኮ ጊዜ የነበራቸውን ሥርዐት አልባ ባሕርይ በተዘዋዋሪ መንገድ መናገሩ ይሆናል (11፥18-22)።

ቈጥርም:: [6]ፍቅር ከእውነት ጋር እንጂ በዐመፅ ደስ አይሰኝም:: [7]ፍቅር ሁልጊዜ ይታገሣል፤ ሁልጊዜ ያምናል፤ ሁልጊዜ ተስፋ ያደርጋል፤ ሁልጊዜ ጸንቶ ይቆማል::

[8]ፍቅር ከቶ አይወድቅም፤ ነገር ግን ትንቢት ቢሆን ይሻራል፤ ልሳንም ቢሆን ይቀራል፤ ዕውቀትም ቢሆን ይሻራል:: [9]ምክንያቱም የምናውቀው በከፊል ነው፤ ትንቢት የምንናገረውም በከፊል ነው:: [10]ነገር ግን ፍጹም የሆነው ሲመጣ በከፊል የነበረው ይሻራል:: [11]ልጅ ሳለሁ እንደ ልጅ እናገር ነበር፤ እንደ ልጅ አስብ ነበር፤ እንደ ልጅም አስላ ነበር:: ከጐለመስሁ በኋላ ግን የልጅነትን ነገር አርግፍ አድርጌ ትቻለሁ:: [12]አሁን የምናየው በመስተዋት ውስጥ እንደሚታይ በድንግዝግዝ ነው፤ በዚያን ጊዜ ግን ፊት ለፊት እናያለን:: አሁን የማውቀው በከፊል ነው፤ በዚያን ጊዜ እኔ ራሴ ሙሉ በሙሉ የታወቅሁትን ያህል ዐውቃለሁ::

[13]እንግዲህ እምነት፣ ተስፋ፣ ፍቅር እነዚህ ሦስቱ ጸንተው ይኖራሉ፤ ከእነዚህም የሚበልጠው ፍቅር ነው::

## የትንቢትና የልሳን ስጦታዎች

**14** ፍቅርን ተከታተሉ፤ መንፈሳዊ ስጦታዎችን፣ በተለይም ትንቢት የመናገርን ስጦታ በብርቱ ፈልጉ:: [2]በልሳን[o] የሚናገር ስለእግዚአብሔር እንጂ ለሰው አይናገርም፤ ምስጢር የሆነውን በመንፈስ[n] ስለሚናገር የሚረዳው የለም:: [3]ትንቢትን የሚናገር ግን ለማነጽ፣ ለማበረታታትና ለማጽናናት ለሰው ይናገራል:: [4]በልሳን የሚናገር ራሱን ያንጻል፤ ትንቢትን የሚናገር ግን ቤተ ክርስቲያንን ያንጻል:: [5]ሁላችሁም በልሳን[w] ብትናገሩ እወዳለሁ፤ ከዚህ ይልቅ ግን ትንቢትን ብትናገሩ እወዳለሁ:: ቤተ ክርስቲያን እንድትታነጽ በልሳን የሚናገር ሰው የተናገረውን ካልተረጐመ፣ በልሳን ከሚናገር ይልቅ ትንቢትን የሚናገር ይበልጣል::

[6]እንግዲህ ወንድሞች ሆይ፤ ወደ እናንተ በምመጣበት ጊዜ፣ በመግለጥ ወይም በዕውቀት ወይም በትንቢት ወይም በትምህርት ካልነገርኋችሁ በልሳን ብናገር ምን እጠቅማችኋለሁ? [7]እንደ ዋሽንትና እንደ በገና ያሉ ሕይወት የሌላቸው ነገሮች እንኳ የድምፃቸው ቃና ልዩነት ከሌለው ዜማቸውን እንዴት ማወቅ ይቻላል? [8]ደግሞም መለከት ትክክል ያልሆነ የጥሪ ድምፅ ካሰማ፣ ለጦርነት ማን ይዘጋጃል? [9]እናንተም እንደዚሁ

13፥6 2ተሰ2፥12፤ 2ዮሐ4፤3ዮሐ3:4
13፥7 ቍ8:13
13፥8 ቍ1:2
13፥9 ቍ12፤ 1ቆሮ 8፥2
13፥10 ፊል3፥12
13፥11 መዝ131፥2
13፥12 ዘፍ32፥30፤ ኢዮ19፥26፤26፥14፤ 36፥26፤1ቆሮ8፥3፤ ገላ4፥9፤1ዮሐ3፥2
13፥13 ማቴ22፥37-40፤ሮሜ5፥2-5፤ 1ቆሮ16፥14፤ገላ5፥5: 6፤ኤፌ4፥2-5፤ ቈላ1፥4:5፤ 1ተሰ1፥3፤5፥8፤ ዕብ6፥10-12፤ 1ዮሐ4፥7-12:16
14፥1 ቍ39፤ 1ቆሮ12፥1:31፤ 16፥ 14፤ኤፌ4፥11
14፥2 ቍ6-11:16፤ ማር16፥17፤1ቆሮ13፥2
14፥3 ቍ4:5:12: 17:26:31፤ ሮሜ14፥19
14፥4 ቍ3፤ ማር16፥17፤ 1ቆሮ13፥2
14፥5 ቍ3፤ ዘኍ11፥29
14፥6 ቍ26፤ ሮሜ6፥17፤2ቆሮ8፥7፤ ኤፌ1፥17
14፥8 ዘኍ10፥9፤ ኤር4፥19

[o]2 *ወይም በሌላ ቋንቋ፤* እንዲሁም ቍ 4:13:14:19:26 እና 27 ይመ
[n]2 *ወይም በመንፈሱ*
[w]5 *ወይም በሌሎች ቋንቋዎች፤* እንዲሁም ቍ6:18:22:23 እና 39 ይመ

13፥6 በዐመፅ ደስ አይሰኝም፤ በም 5 ላይ ያደርጉት እንደ ነበረው ነው::

13፥8 *ትንቢትም ቢሆን ይሻራል፤ ልሳንም ቢሆን ይቀራል፤ ዕውቀትም ቢሆን ይሻራል፤* እነዚህ ሦስቱ የከፊልነት ባሕርይ ስላላቸው (ቍ 9) ይቀራሉ፤ ፍጹም የሆነው ነገር በመጣ ጊዜ ግን አስፈላጊዎች አይሆኑም (ቍ10)::

13፥10 *ፍጹም የሆነው፤* ለዚህ ሐረግ የገባው የግሪኩ ቃል፣ "መጨረሻን"፣ "ፍጻሜን"፣ "ሙሉነትን" ወይም "ብስለትን" ሊያመለክት ይችላል፤ በዚህ ዐውደ ምንባብ ውስጥ ንጽጽሩ ከፊል በሆነውና ሙሉ በሆነው መካከል ነው:: አንዳንዶች ይህ ሐረግ የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ያመለክታል ይላሉ፤ ሌሎች ከክርስቲያኖች መሞት ጋር ያዛምዱታል፤ ሌሎች ደግሞ ከቤተ ክርስቲያን መመሥረት ጋር ያያይዙታል (ቍ 11 ማብ ይመ)፤ የተቀሩት ደግሞ ከአዲስ ኪዳን መጽሐፍት መጻፍና ተቀባይነት ማግኘት ጋር ያዛምዱታል:: ይሁን እንጂ በቍ 12 ላይ ጳውሎስ የሚናገረው ስለ ጌታ ዳግም ምጽአት ይመስላል::

13፥12 *አሁን የምናየው በመስተዋት ውስጥ እንደሚታይ በድንግዝግዝ ነው፤* በምስያነት የቀረበው የተወለወለ የፊት መመልከቻ ብረት ነው (ናስ ሊሆን ይችላል)፤ በዚህ ዐይነት መመልከቻ አንድ ሰው ፊቱን ማየት የሚችለው ጥራት በሌለው መልክ ነው (ከያዕ 1፥23 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይህም የተነጻጸረው ጌታን በሰማይ ግልጽ በሆነ መንገድ ከማየት ጋር ነው:: ሙሉ በሙሉ የታወቅሁትን ያህል ዐውቃለሁ፤ ጌታ አንድን አማኝ ሙሉ በሙሉ የሚያውቀውን ያህል ውሱን የሆነም አማኝ ጌታን በዚያ ልብ ያወቀዋል:: ይህ ግን ጌታ ዳግም እስከሚመጣ ድረስ እውን አይሆንም::

13፥13 *እምነት፣ ተስፋ፣ ፍቅር፤* የ1ተሰ 1፥3 ማብ ይመ:: *ጸንተው ይኖራሉ፤* አሁንም፣ ለዘላለምም ነው:: *ከእነዚህም የሚበልጠው ፍቅር ነው፤* እግዚአብሔር ፍቅር ስለ ሆነ (1ዮሐ 4፥8)፣ ፍቅሩንም ስለ ገለጠልንና (1ዮሐ 4፥10) እርስ በርስ እንድንዋደድ ስላዘዘን (ዮሐ 13፥34-35) ነው:: ፍቅር ለዘላለም ነዋሪ በመሆኑ፣ ከስጦታዎች ሁሉ ይበልጣል:: እነዚህ ሰው ሁሉ ሲሻቸው የነበሩ ስጦታዎች ካለፉ በኋላ እንኳ፣ ፍቅር በእግዚአብሔርና በተዋጀ ሕዝቡ መካከል ጸንቶ የሚያኖር ሕግ ነው::

14፥1-5፤ እዚህ ላይ ጳውሎስ አጽንቶ የሚናገረው መሠረታዊ መርሕ፣ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የሚደረገው ማናቸውም ነገር አካሉን የሚያንጽ መሆን አለበት የሚል ነው፤ ይህም በ 12፥7 ላይ፣ "... የሚሰጠው ለጋራ ጥቅም ነው" ከሚለው ጽኑ አቋምና በም 13 ላይ ከተገለጸው ከፍቅር መርሕ ጋር ይስማማል:: በዚህ መሠረት በቤተ ክርስቲያን የሚነገረው ሁሉ፣ ማንኛውም ሰው በሚሰማው ቋንቋ መሆን አለበት፤ በሕዝቡ ቋንቋ መነገሩ አስፈላጊ ነው፤ ይህ ካልሆነ ግን በሕዝቡ ቋንቋ መተርጐም አለበት፤ እንግዲህ የተነገረውን ልሳን የሚተረጕም ከሌለ፣ ከልሳን ይልቅ ትንቢት ይመረጣል፤ ምክንያቱም ትንቢት የሚነገረው በሰሚዎቹ ቋንቋ ነው::

14፥1 *ፍቅርን ተከታተሉ፤ መንፈሳዊ ስጦታዎችን፤* መንፈሳዊ ስጦታዎች ፍሬያማ የሚሆኑት፣ በፍቅር አማካይነት ስንጠቀምባቸው ነው:: *በተለይም ትንቢት የመናገርን ስጦታ፤* የ12፥10 ማብ ይመ::

14፥2 *በልሳን፤* በሌላ ቋንቋ ማለት ነው:: በልሳን የሚናገረው ሰው ምን እንደተናገረ አድማጮቹ ሊረዱ አይችሉም፤ ስለዚህ እርሱ የሚናገረው ካልተተረጐመ በቀር ለሌሎች ምስጢር ይሆናል፤ የሚረዳው እግዚአብሔር ብቻ ይሆናል:: *በመንፈስ፤* የሚናገረው በአእምሮው አይደለም ማለት ነው (ቍ 14-17 ይመ)::

*14፥3፤* ትንቢት የሚናገር ሰው ሌሎችን ያንጻል (12፥7)::

14፥4 *ራሱን ያንጻል፤* በልሳን የሚናገር ሰው የሚናገረውን ስለማያስተውል፣ ይህ መታነጽ አእምሮን አያሳትፍም:: መታነጹ በግል ሕይወት ደረጃ ነው:: ይህም በስሜት፣ እምነትን በማጽናት፣ የበለጠ ራስን በመስጠትና በፍቅር በመጕልበት አኳያ ነው::

14፥5 *ካልተረጐመ፤* በልሳን የሚናገረው ሰው የመተርጐም ስጦታ ካለው፣ የሚናገረውን ሰው ስለሚረዳው የትንቢትን ያህል ጠቃሚ ነው (ቍ 13 ይመ):: *በልሳን ብትናገሩ እወዳለሁ፤* በሥርዐት እስከ ሆነ ድረስ፣ ጳውሎስ በልሳን መናገርን አልተቃወመም:: *ትንቢትን የሚናገር ይበልጣል፤* የሚናገረውን ሰው ሁሉ ስለሚያስተውለውና ቤተ ክርስቲያንን የሚያንጽ በመሆኑ፣ ለጋራ ጥቅም አስፈላጊ ነው::

14፥6 *ምን እጠቅማችኋለሁ?* በልሳን የተነገረው ተተርጕሞ ቤተ ክርስቲያን ካልተረዳችውና ካልታነጸችበት፣ አንድ ሰው በልሳን መናገሩ ጥቅም የለውም::

14፥7 *እንደ ዋሽንትና እንደ በገና፤* በግሪክ ኅብረተ ሰብ ዘንድ የታወቁ የዜማ መሣሪያዎች ነበሩ:: *የድምፃቸው ቃና ልዩነት ከሌለው፤* አንድ ሰው የዜማን ቃና ለይቶ እንዲያውቅና እንዲያጣጥም ከተፈለገ፣ የተለያዩ የድምፅ ቃናዎች መኖር አለባቸው፤ እነዚህ የድምፅ ቃናዎች ትርጕም ባለው መልክ መቀናጀት ይኖርባቸዋል:: አንድ የድምፅ ቃና ብቻ ቢደጋገም ጣዕም አይኖረውም::

14፥8 *መለከት... ለጦርነት ማን ይዘጋጃል?* መለከት ሲነፋ ለጦርነት ተዘጋጁ ማለት እንደሆነ በግሪኮች ዘንድ የታወቀ ነበር፤

ናችሁ፤ ከአንደበታችሁ ትርጕም ያለው ቃል ካልወጣ፣ የምትናገሩትን ማን ሊያስተውለው ይችላል? ለነፋስ የምትናገሩ ትሆናላችሁ። [10]በዓለም ላይ ብዙ ዐይነት ቋንቋዎች አሉ፤ ትርጕም የሌለውም ቋንቋ የለም። [11]እንግዲህ አንድ ሰው የሚናገረውን ቋንቋ ትርጕሙን ካላወቅሁ፣ ለሚናገረው እንግዳ እሆንበታለሁ፤ እርሱም ለእኔ እንግዳ ይሆንብኛል። [12]እናንተም እንደዚሁ ናችሁ፤ መንፈሳዊ ስጦታዎችን ለማግኘት የምትሹ በመሆናችሁ፣ ቤተ ክርስቲያን የምትታነጽበትን ስጦታዎች ለማግኘት ይበልጥ ፈልጉ።

[13]ስለዚህ በልሳን የሚናገር ሰው የሚናገረውን መተርጐም እንዲችል ይጸልይ። [14]በልሳን በምጸልይበት ጊዜ መንፈሴ ይጸልያል፤ አእምሮዬ ግን ያለ ፍሬ ነው። [15]ታዲያ፣ ምን ማድረግ አለብኝ? በመንፈስ እጸልያለሁ፤ በአእምሮም ደግሞ እጸልያለሁ፤ በመንፈስ እዘምራለሁ፤ በአእምሮም ደግሞ እዘምራለሁ። [16]እንዲህማ ካልሆነ እግዚአብሔርን በመንፈስ በምታመሰግንበት ጊዜ፣ ለነገሩ እንግዳ የሆነ ሰው[ሀ] አንተ የምትናገረውን ካልተረዳ፣ እንዴት አድርጎ ለምስጋናህ፣ "አሜን" ሊል ይችላል? [17]አንተ በሚገባ ታመሰግን ይሆናል፤ ሌላው ሰው ግን አይታነጽበትም።

[18]ከሁላችሁ የበለጠ በልሳን ስለምናገር እግዚአብሔርን አመሰግናለሁ። [19]ነገር ግን በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሌሎችን ለማስተማር፣ ዐሥር ሺህ ቃላት በልሳን ከምናገር ይልቅ፣ አምስት ቃላት በአእምሮዬ ብናገር ይሻላል።

[20]ወንድሞች ሆይ፤ በአስተሳሰባችሁ ሕፃናት አትሁኑ፤ ለክፉ ነገር ሕፃናት ሁኑ፤ በአስተሳሰባችሁ ግን ጕልማሶች ሁኑ። [21]በሕግም እንዲህ ተብሎ ተጽፎአል፤

"ቋንቋቸው እንግዳ በሆነ ሰዎች፣
 በባዕዳንም አንደበት፣
ለዚህ ሕዝብ እናገራለሁ፤
 ይህም ሆኖ አይሰሙኝም"
  ይላል ጌታ።

[22]ስለዚህ በልሳን መናገር ለማያምኑ የሚሆን ምልክት እንጂ ለሚያምኑ አይደለም፤ ትንቢት ግን ለሚያምኑ እንጂ ለማያምኑ አይደለም። [23]እንግዲህ የቤተ ክርስቲያን ምእመናን በአንድነት በተሰበሰቡበት፣ ሁሉም በልሳን በመናገር ላይ ሳሉ፣ እንግዶች[ለ] ወይም የማያምኑ ሰዎች ወደ ጉባኤው ቢገቡ፣ አብደዋል አይሉምን? [24]ነገር ግን ሁሉም ትንቢት በመናገር ላይ ሳሉ፣ እንግዳ[ሐ] ወይም የማያምን ሰው ቢገባ፣ በሁሉ ይወቀሳል፤ በሁሉ ይመረመራል፤ [25]በልቡም የተሰወረው ነገር ይገለጣል፤ እንዲሁም፣ "እግዚአብሔር በእርግጥ በመካከላችሁ ነው" በማለት በግንባሩ ተደፍቶ ለእግዚአብሔር ይሰግዳል።

## ሥርዐት ያለው አምልኮ

[26]ወንድሞች ሆይ፤ እንግዲህ ምን እንበል? በምትሰበሰቡበት ጊዜ እያንዳንዱ መዝሙር

[ሀ]16 ወይም *ከሚጠይቁት መካከል*
[ለ]23 ወይም *አንዳንድ የሚጠየቁ*
[ሐ]24 ወይም *የሚጠይቅ*

14፥11 ዘፍ11፥7
14፥12 ቍ3፤ 1ቆሮ12፥1
14፥13 ቍ5
14፥14 ቍ2
14፥15 ቍ2:14፤ ኤፌ5፥19
14፥16 ዘዳ27፥15-26፤1ዜና16፥36፤ ነህ8፥6፤መዝ106፥48፤ማቴ14፥19፤ 1ቆሮ11፥24፤ ራእ5፥14፤7፥12
14፥17 ቍ3
14፥19 ቍ6
14፥20 ኤር4፥22፤ ማቴ10፥16፤ ሮሜ16፥19፤ 1ቆሮ3፥1፤ኤፌ4፥14፤ዕብ5፥12:13፤ 1ጴጥ2፥2
14፥21 ቍ34፤ ዘዳ28፥49፤ኢሳ28፥11:12፤ዮሐ10፥34
14፥22 ቍ1
14፥23 ሐሥ2፥13
14፥25 ኢሳ45፥14፤ ዘካ8፥23፤ሮሜ2፥16
14፥26 ቍ2:6፤ ሮሜ7፥1፤14፥19፤ 1ቆሮ12፥7-10፤ ኤፌ5፥19

አይሁድም ከበግ ቀንድ የተሠራው መለከት ለምን አገልግሎት እንደሚውል ያውቁ ነበር (ዘኍ 10፥9፤ ኢያ 6፥4:9)። ደግሞም ከመሣሪያዎቹ የሚወጣው ድምፅ አንድ መልእክት ማስተላለፍ አለበት።

14፥9 *ትርጕም ያለው ቃል ካልወጣ፤* በልሳን ሳይሆን አድማጮቹ በሚናገሩት ቋንቋ ተናገሩ ማለቱ ነው (አለበለዚያ በልሳን የተነገረው ይተርጐም)።

14፥10 ብዙ ዐይነት ቋንቋዎች፤ አንዳንዶች በቍ 10-11 ላይ የተነገረውን የሚረዱት ከም 12-14 ባለው ክፍል የተወሳው "ልሳን" ከዚህ በፊት የማይታወቅ ባዕድ ቋንቋ እንደ ሆነ አድርገው ነው።

14፥12 *ቤተ ክርስቲያን የምትታነጽበትን ስጦታዎች ለማግኘት ይበልጥ ፈልጉ፤* የም 14 መሠረታዊ መርሕም ነው።

14፥14 *አእምሮዬ ግን ያለ ፍሬ ነው፤* አንድ ሰው በልሳን ሲናገር ወይም በልሳን ሲጸልይ አእምሮው ትርጕም ያለው ቋንቋ አያመነጭም።

14፥15-17 *እጸልያለሁ... እዘምራለሁ ... እግዚአብሔርን ... በምታመሰግንበት ጊዜ ... ለምስጋናህ፣ "አሜን" ሊል፤* በብሉይ ኪዳንና (1ዜና 16፥36፤ ነህ 5፥13፤ 8፥6፤ መዝ 104፥33፤ 136፥1፤ 148፥1) በአዲስ ኪዳን (ሮሜ 11፥36፤ ኤፌ 5፥18-20) የሚገኙ የአምልኮ መግለጫዎች ናቸው። "አሜን" ማለት፣ "እውነት ነው" ወይም፣ "ይሁን" ማለት ሲሆን፣ አማኙ በሰማው ነገር ተስማምቶ መቀበሉን ያመለክታል (ከገላ 1፥5፤ ጋር ያነጻጽሩ)። ስለዚህ በልሳን የመጣው መልእክት መተርጐም አለበት።

14፥15 *በመንፈስ እጸልያለሁ፤ በአእምሮም... በመንፈስ እመዘምራለሁ፤ በአእምሮም፤* ጳውሎስ አንዳንድ ጊዜ በመንፈስ በልሳን ይጸልያል ወይም ይዘምራል፤ ሌላ ጊዜ ደግሞ በአእምሮው በራሱ ቋንቋ ይጸልያል ወይም ይዘምራል ማለት ሊሆን ይችላል። አንዳንዶች ደግሞ ጳውሎስ በአእምሮውም በመንፈሱም በአንድ ጊዜ እንደሚጸልይ ወይም እንደሚዘምር መግለጹ ነው ይላሉ።

14፥19 *ነገር ግን በቤተ ክርስቲያን ውስጥ፤* አንዳንዶች የልሳን ስጦታ ለግል ጸሎት በሚውልበት ጊዜ፣ መተርጐም አያስፈልግም ይላሉ። መተርጐም አያስፈልግም የሚሉትም ቍ 18ን እዚህ ላይ ከተጠቀሰው ጋር በማነጻጸር ነው (ቍ 14 ይመ)።

14፥20 *ለክፉ ነገር ሕፃናት ሁኑ፤* ሕፃናት ከሌላው በልጦ ለመታየት እንደማይመኙ ሁሉ፤ እናንተም ከሌሎች ለመብለጥ ስትሉ መንፈሳዊ ስጦታዎችን (ለምሳሌ በልሳን መናገርን) ለማግኘት ክፉ ምኞት ወይም ሐሳብ አይደርባችሁ ማለቱ ነው።

*14፥21-22፤* ከኢሳ 28 የተጠቀሰው ይህ ክፍል፣ የአሦራውያን ባዕድ ቋንቋ፣ በማያምኑት እስራኤላውያን ላይ ፍርድ እንደሚመጣ የሚያሳይ ምልክት ነበር። ጳውሎስ ከዚህ እውነታ በመነሣት በልሳን የመናገር ዐላማ ለማያምኑ ምልክት እንደሆነ ይናገራል (ቍ 22)፤ ለዚህም በሐሥ 2፥4-12 ላይ ያለው ታሪክ አንዱ ምሳሌ ነው። ትንቢትም ደግሞ የተገለጠውን እውነት ለመቀበል ዝግጁ ለሆኑ ሁሉ (ከማቴ 13፥11-16 ጋር ያነጻጽሩ) መልእክትን ስለሚያስተላልፍ ለሚያምኑ ሰዎች ምልክት ነው (ቍ 22)።

14፥21 *በሕግም፤* ጳውሎስ በሮሜ 3፥10-19 ትንቢተ ኢሳይያስን ጨምሮ ከብዙ የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ከጠቀሰ በኋላ በቍ 19 ላይ ሁሉንም በአንድነት፣ "ሕግ" ይላቸዋል።

14፥23 *እንግዶች፤* የወንጌልን ሐሳብ ያልተረዱና እውነትን ፍለጋ ላይ ያሉ ሰዎች ሊሆኑ ይችላሉ። *የማያምኑ ሰዎች፤* ወደ ድነት ለመምጣት ፈቃደኝነት ያላሳዩ ናቸው። ዐውደ ምንባቡ የሚያሳየው እያንዳንዱ ሰው በልሳን ከመናገሩ የተነሣ ውዥምብር የሰፈነበትን የምእመናን ጉባኤ ነው። *አብደዋል፤* ውዥምብሩ እንግዳ የሆነውን ሰው ያስበረግጋል፤ ደግሞም ሌሎችን ይስባል ተብሎ የተደረገው ነገር ባልዳኑ ሰዎች ላይ አሉታዊ ተጽዕኖ ያስከትላል።

14፥24 ሁሉም ትንቢት በመናገር ላይ ሳሉ፤ ለሚያምኑት ተብሎ በአገሬው ቋንቋ የተነገረው ትንቢት በማያምኑት ላይ አዎንታዊ ተጽዕኖ ያስከትላል፤ ምክንያቱም የተነገረውን ትንቢት ሰምተው ስለሚረዱ በኀጢአታቸው ይወቀሳሉ (ይሁን እንጂ ትንቢት በመናገር ላይ የተጣለውን ገደብ በቍ 29-32 ላይ እና ማብ ይመ)።

14፥26-27 *እያንዳንዱ ... ሌላው ደግሞ፤* እዚህም ላይ በአጽንዖት የተገለጸው፣ መንፈሳዊ ስጦታዎች የተለያዩና ተደጋጋፊ

አለው፤ ትምህርት አለው፤ መግለጥ አለው፤ በልሳን መናገር አለው፤ መተርጐም አለው። ይህ ሁሉ ግን ለማነጽ ይሁን። [27]በልሳን የሚናገር ቢኖር፣ ሁለት ወይም ቢበዛ ሦስት በየተራ ይናገሩ፤ ሌላው ደግሞ ይተርጒም፤ [28]የሚተረጒም ሰው ከሌለ ግን በጉባኤ መካከል ዝም ይበልና፤ ለራሱና ለእግዚአብሔር ይናገር።

[29]ሁለት ወይም ሦስት ነቢያት ይናገሩ፤ ሌሎቹ ደግሞ የተነገረውን በጥንቃቄ ይመዝኑ። [30]ከተቀመጡትም መካከል አንድ ሰው አንድ ነገር ቢገለጥለት፣ የመጀመሪያው ተናጋሪ ዝም ይበል። [31]እያንዳንዳችሁ እንድትማሩና እያንዳንዳችሁ እንድትበረታቱ፣ ሁላችሁ በየተራ ትንቢት መናገር ትችላላችሁ። [32]የነቢያት መናፍስት ለነቢያት ይታዘዛሉ፤ [33]እግዚአብሔር የሰላም አምላክ እንጂ የሁከት አምላክ አይደለም።

በቅዱሳን አብያተ ክርስቲያናት ሁሉ እንዲሁ ነው፣ [34]ሴቶች በጉባኤ ዝም ይበሉ፤ ሕግም እንደሚለው እንዲታዘዙ እንጂ እንዲናገሩ አልተፈቀደላቸውም፤ [35]ሴቶች ለማወቅ የሚፈልጉት አንዳንድ ነገር ካለ፣ ባሎቻቸውን በቤት ይጠይቁ፤ ምክንያቱም ሴት በጉባኤ መካከል ብትናገር የሚያሳፍር ነው።

[36]የእግዚአብሔር ቃል የወጣው ከእናንተ ነውን? ወይስ የደረሰው ወደ እናንተ ብቻ ነውን? [37]ማንም ነቢይ ነኝ የሚል ወይም መንፈሳዊ ስጦታ አለኝ የሚል ቢኖር፣ ይህ የጻፍሁላችሁ የጌታ ትእዛዝ መሆኑን ይወቅ፤ [38]ይህን የማያውቅ ቢሆን ግን እርሱም አይታወቅ።[1]

[39]ስለዚህ፣ ወንድሞች ሆይ፤ ትንቢት ለመናገር በብርቱ ፈልጉ፤ በልሳን መናገርንም አትከልክሉ፤ [40]ነገር ግን ሁሉም በአግባብና በሥርዐት ይሁን።

14፥29 ቍ32፡37፤ 1ቆሮ12፥10፤13፥2
14፥32 1ዮሐ4፥1
14፥33 ቍ40፤ ሐሥ9፥13፤ ሮሜ15፥33፤ 1ቆሮ7፥17፤10፥32
14፥34 ቍ21፤ ዘፍ3፥16፤1ቆሮ11፥5፡ 13፤ኤፌ5፥22፤ 1ጢሞ2፥11፡12
14፥36 ዕብ12
14፥37ሐሥ11፥27፤ 1ቆሮ13፥2፤2፥15፤ 12፥1፤2ቆሮ10፥7፤ 1ዮሐ4፥6
14፥39 ቍ1፤ 1ቆሮ12፥31፤ኤፌ4፥11
14፥40 ቍ33፤ ቈላ2፥5

[1]38 አንዳንድ ቅጆች፣ ይህን ለማወቅ የማይፈልግ ቢሆን እርሱም አይታወቅ ይላሉ።

ባሕርይ ያላቸው መሆኑ ነው፤ የተወሰኑ መሪዎች ወይም አለቆች ብቻ ሳይሆኑ፣ አማኞች ሁሉ በተሰጣቸው ስጦታ ማገልገል እንደሚችሉ ግልጽ ነው።

14፥26 *መዝሙር ... ትምህርት... መግለጥ ... ልሳን ... መተርጐም፤* በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን የነበሩ የአምልኮ መግለጫዎች ናቸው። ከእነዚህም መካከል አንዳንዶቹ (መዝሙርና ትምህርት) ከብሉይ ኪዳንና ከምኵ ራብ አምልኮ የተወረሱ ናቸው (ከማቴ 26፥30፤ ሉቃ 4፥16-22 *ጋር ያነጻጽሩ*)። ማንኛውም ክርስቲያናዊ የአምልኮ መግለጫ ቤተ ክርስቲያንን የሚያንጽ መሆን አለበት።

14፥27-28፤ "በጉባኤ" (በቤተ ክርስቲያን) ውስጥ (ቍ 28) ልሳን ሲነገር ሦስት ገደቦች አሉ (1) በጉባኤ ላይ ሁለት ወይም ሦስት ብቻ መናገር ይኖርባቸዋል፤ (2) እነርሱም ተራ በተራ መናገር አለባቸው፤ (3) በልሳን የተነገረው መተርጐም አለበት።

14፥28 *ዝም ይበል፤* በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ በልሳን የሚናገር ሰው፣ በጉባኤው ውስጥ ሌላ ተርጓሚ መኖሩን ማረጋገጥ ያለበት ይመስላል።

14፥29 *ሁለት ወይም ሦስት ነቢያት ይናገሩ፤* በልሳን የሚናገሩት እንደሚያደርጉት ሁሉ (ቍ27)፣ እነዚህም ተራ በተራ (ቍ 31) መናገር እንዳለባቸው ግልጽ ነው። *በጥንቃቄ ይመዝኑ፤* የተነገረውን ያልዩ፤ ይመርምሩ። ነቢያት ራሳቸው የሌላውን ነቢይ ትንቢት ጠቀሜታ መመዘን አለባቸው (የቍ 32 ማብ ይመ)።

14፥30 *ቢገለጥለት፤* በቅዱሳት መጻሕፍት ላይ እንዲታከል የተሰጠ መገለጥ አይደለም። በብሉይ ኪዳን ዘመን በቅዱሳት መጻሕፍት የሰፈረው መገለጥ የመጣው በነቢያት በኩል ሲሆን፣ በአዲስ ኪዳን ደግሞ በሐዋርያትና በቅርብ አጋሮቻቸው አማካይነት ነው። በም 12-14 ላይ የተመለከተው ትንቢት ግን፣ በማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባል በኩል ሊመጣ ይችላል (ቍ 26፡29-31)። ትንቢቱም ወደ ፊት የሚሆነውን አስቀድሞ መናገር (አጋቦስ፣ ሐሥ 11፥28፤ 21፥10-11) ወይም መለኮታዊ ምሪት ለመስጠት (ሐሥ 13፥1-2)ወይም ደግሞ ለማበረታታት፣ ለማደፋፈር ወይም ለማጽናናት የመጣ መልእክት ሊሆን ይችላል (ቍ 3)።

14፥32 *ለነቢያት ይታዘዛሉ፤* ትንቢትን መናገር (በልሳን መናገርም ቢሆን) ከቍጥጥር ውጭ የሚሆን ስሜታዊነት አይደለም፤ እነዚህ ስጦታዎች በተቀባዮቹ ቍጥጥር ሥር መዋል እንዳለባቸው ጳውሎስ በአጽንዖት ይገልጻል (ቍ 15፡26-32)። የቍ27-29 ማብ ይመ።

14፥33 *እግዚአብሔር የሰላም አምላክ፤* የ1ተሰ 5፥23 ማብ ይመ። *የሁከት፤* ጳውሎስ ሥርዐት አልባውና ቅጥ ያጣው የቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን አምልኮ፣ ወደ ክርስቶስ ሰላምና አንድነት የጠራቸውን የእግዚአብሔርን ስም ያሰድባል የሚል ሥጋት አድሮበት ነበር። *በቅዱሳን አብያተ ክርስቲያናት ሁሉ፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ ለየት ያለ አገላለጽ ሲሆን፣ በዚህች ምድር ያሏቸው የእግዚአብሔር ቤተክርስቲያን ሁለንታዊ ባሕርይ እንዳላት በአጽንዖት ያመለክታል፤ አብያተ ክርስቲያናት ሁሉ ቀጥሎ የተሰጠውን መመሪያ መታዘዝ ይኖርባቸዋል።

*14፥34-35፤* የ11፥3-16 ማብ ይመ። አንዳንዶች 11፥3ን በመጥቀስ፣ ለአስተዳደርም ሆነ ለሥልጣን መሠረት የሚሆን እግዚአብሔር የደነገገው ሥርዐት እንዳለ ያምናሉ። ተወልደው ያደጉበት ባህል የተለያየ ቢሆንም፣ ሴቶች በቤታቸውም ሆነ (ኤፌ 5፥22 ይመ) በቤተ ክርስቲያን (ቍ 34፤ 1ጢሞ 2፥11-12 ይመ) ለባሎቻቸው መታዘዝ አለባቸው። በዚህ አመለካከት መሠረት፣ ምን ጊዜም ተፈጻሚነት ያለው ሥርዐት በሥነ ፍጥረት ጊዜ ተደንግጐአል (የ11፥ 5-6 ማብ ይመ)።

አንዳንዶች ደግሞ እዚህ ላይ የጳውሎስ ትኩረት ክርስቲያኖች በተሰጣቸው መንፈሳዊ ስጦታ ሲያገለግሉ ሌሎችንና (ቍ 30-31 ይመ) እግዚአብሔርን (ቍ 33 ይመ) ካከበሩ ቤተ ክርስቲያን ትጠነክራለች (ቍ 26) የሚለው ላይ ነው ይላሉ። እንዲህ ያለው አክብሮት የማኅበረ ሰቡን ወግና ልማድ መከተል አለበት። በአንድ ማኅበረ ሰብ ልማድ አንዲት ሴት በቤተ ክርስቲያን በሕዝብ ፊት ቆማ መናገሯ የሚያሳፍር ተግባር ከሆነ (በእርግጥ በቆሮንቶስ የሚያሳፍር ነበር፤ ቍ 35)፣ እንዲህ ማድረጓ አለማክበሯን ስለሚያሳይ ዝም ማለት አለባት። በቆሮንቶስም ልማድ ቢሆን ሴት በቤተ ክርስቲያን ቆማ የምትናገርበት ሁኔታ ነበር፤ ለምሳሌ በ 11፥5 ሴቶች በአምልኮ ጊዜ በሕዝብ ፊት መጸለይና ትንቢት መናገር እንደሚችሉ ጳውሎስ ተናግሯል። በዚህ አመለካከት መሠረት የጳውሎስ ዐላማ ሴቶች በቤተ ክርስቲያን ስላላቸው ሚና መወሰን ሳይሆን፣ በአምልኮ ጊዜ ሁሉም ነገር በአግባብና (ቍ 34-35) በሥርዐት (ቍ27-31) መሆን አለበት የሚል ነው (ቍ 40)።

ሌሎች ደግሞ በዚህ ክፍል ጳውሎስ የሚናገረው ልሳንና ትንቢት በሚነገርበት ጊዜ፣ ሴቶች ሁኔታውን በማጀብ በአምልኮ ላይ ስለሚፈጥሩት ሁካታ ነው ይላሉ። ሴቶች ስለ ጒዳዩ ማብራሪያ ፈልገው በሕዝብ ፊት ሁካታ ከሚፈጥሩ፣ በቤታቸው ከባሎቻቸው ጋር ሊነጋገሩበት ይገባል (ከቍ35 *ጋር ያነጻጽሩ*)። ጳውሎስ ሴቶች በቤተ ክርስቲያን ፈጽሞ መናገር የለባቸውም አላላም (ቍ 11፥5 ይመ)። ጳውሎስ የከለከለው በእነዚህ ቍጥሮች ላይ የተመለከተውን ሥርዐት አልባ ንግግር ነው።

*14፥36፤* የቆሮንቶስ ሰዎች በዚህ ጒዳይ እንደ እግዚአብሔር ቃል በመመላለስ ፈንታ የራሳቸውን ልማድ ይከተሉ እንደ ነበር ለማመልከት፣ ጳውሎስ እነዚህን ጥያቄዎች በሥላቅ መልክ ያቀርብላቸዋል።

14፥37 *የጌታ ትእዛዝ፤* ጳውሎስ የሰጠው ትእዛዝ የጌታን ትእዛዝ በመሆኑ መከበር ይኖርበታል። መንፈሳዊ ስጦታዎች እንደ ዋና ነገር በሚቈጠሩበት ስፍራ እውነተኛ ስጦታ የተቀበለ ሰው ሐዋርያው ከእግዚአብሔር ያገኘውን ሥልጣን እንዲቀበል ጳውሎስ በአጽንዖት ይናገራል።

14፥38 *እርሱም አይታወቅ፤* ጳውሎስና አብያተ ክርስቲያናት እንዲህ ያለውን የማይታዘዝ ሰው አይቀበሉትም፤ በዚህም ምክንያት አማኝ እንዳልሆነ ይቈጠራል።

14፥39 *በልሳን መናገርንም አትከልክሉ፤* በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን በልሳን በመናገር ምክንያት ለተፈጠረው ችግር ጳውሎስ የሰጠው መፍትሔ በልሳን እንዳይናገሩ መከልከል ሳይሆን፣ ፈር የለቀቀውን የስጦታውን አጠቃቀም ማረምና ሥርዐት ማስያዝ ነበር።

14፥40 *በአግባብና በሥርዐት፤* በቍ 26-35 ላይ እንደ ተዘረዘረው ነው።

## የክርስቶስ ትንሣኤ

**15** አሁንም፣ ወንድሞች ሆይ፤ የሰበክሁላችሁንና የተቀበላችሁትን ደግሞም ጸንታችሁ የቆማችሁበትን ወንጌል ላሳስባችሁ እወዳለሁ፤ [2]የሰበክሁላችሁን ቃል አጥብቃችሁ ብትይዙ፣ በዚህ ወንጌል ትድናላችሁ፤ አለዚያ ያመናችሁት በከንቱ ነው።

[3]እኔ የተቀበልሁትንና ከሁሉ በላይ የሆነውን[ጣ] ለእናንተ አስተላልፌአለሁ፤ ቅዱሳት መጻሕፍት እንደሚሉት ክርስቶስ ስለ ኀጢአታችን ሞተ፤ [4]ተቀበረ፤ በቅዱሳት መጻሕፍት እንደ ተጻፈው ም በሦስተኛው ቀን ተነሣ፤ [5]ከዚያም ለኬፋ[ጨ] ታየ፤ ቀጥሎም ለዐሥራ ሁለቱ ታየ፤ [6]ከዚያም በኋላ ከአምስት መቶ በላይ ለሚሆኑ ወንድሞች በአንድ ጊዜ ታየ፤ ከእነዚህም አብዛኞዎቹ በሕይወት አሉ፤ አንዳንዶቹ ግን አንቀላፍተዋል። [7]ከዚያም ለያዕቆብ ታየ፤ በኋላም ለሐዋርያት በሙሉ ታየ፤ [8]ከሁሉም በኋላ እንደ ጭንጋፍ ለምቈጠር ለእኔ ደግሞ ታየ።

[9]እኔ ከሐዋርያት ሁሉ የማንስ፣ ሐዋርያ ተብዬ ልጠራ እንኳ የማይገባኝ ነኝ፤ ምክንያቱም የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን አሳድጃለሁ፤ [10]ነገር ግን በእግዚአብሔር ጸጋ አሁን የሆንሁትን ሆኛለሁ፤ ለእኔም የተሰጠኝ ጸጋ ከንቱ አልሆነም፤ እንዲያውም ከሁሉም በላይ በትጋት ሠርቻለሁ፤ ዳሩ ግን እኔ ሳልሆን ከእኔ ጋር ያለው የእግዚአብሔር ጸጋ ነው። [11]እንግዲህ እኔም ሆንሁ እነርሱ የምንሰብከው ይህንኑ ነው፤ እናንተም ያመናችሁት ይህንኑ ነው።

## የሙታን ትንሣኤ

[12]ክርስቶስ ከሙታን እንደ ተነሣ የሚሰበክ ከሆነ፣ ከእናንተ አንዳንዶቹ እንዴት የሙታን ትንሣኤ የለም ይላሉ? [13]የሙታን ትንሣኤ ከሌለማ ክርስቶስም አልተነሣም ማለት ነዋ!። [14]ክርስቶስም ካልተነሣ ስብከታችን ዋጋ ቢስ ነው፤ እምነታችሁም ከንቱ ነው። [15]ከዚህም በላይ፣ እግዚአብሔር ክርስቶስን ከሞት አስነሥቶታል ብለን በመመስከራችን፣ ሐሰተኞች የእግዚአብሔር ምስክሮች ሆነን ተገኝተናል፤ ሙታን የማይነሡ ከሆነ፣ ክርስቶስንም አላስነሣውም ማለት ነው፤ [16]ምክንያቱም ሙታን ካልተነሡ፣ ክርስቶስም አልተነ

15፥1 ኢሳ40፥9፤ ሮሜ2፥16፤1ቆሮ3፥6፤ ገላ1፥8
15፥2 ሮሜ1፥16፤ 11፥22
15፥3 ኢሳ53፥5፤ ማቴ26፥24፤ ሉቃ24፥27፤24፥44፤ ዮሐ1፥29፤ሐሥ17፥2፤ 26፥ 22:23፤ 1ቆሮ11፥2፤ገላ1፥4:12፤ 1ጴጥ2፥24
15፥4 ማቴ16፥21፤ 27፥59:60፤ዮሐ2፥21: 22፤ሐሥ2፥24:25: 30:31
15፥5 ማር16፥14፤ ሉቃ24፥34:36-43
15፥6 ቍ18:20፤ ማቴ 9፥24
15፥7 ሉቃ24፥33: 36:37፤ሐሥ1፥3:4፤ 15፥13
15፥8 ሐሥ9፥3-6: 17፤1ቆሮ9፥1፤ገላ1፥16
15፥9 ሐሥ8፥3፤ 1ቆሮ10፥32፤ 2ቆሮ12፥11፤ ኤፌ3፥8፤1ጢሞ1፥15
15፥10 ሮሜ3፥24፤ 12፥3፤2ቆሮ11፥23፤ ፊል2፥13፤ቈላ1፥29
15፥11 ገላ2፥6
15፥12 ቍ4፤ ዮሐ11፥24፤ሐሥ17፥32፤23፥8፤2ጢሞ2፥18
15፥14 1ተሰ4፥14
15፥15 ሐሥ2፥24

ጣ3 ወይም፣ *ከሁሉ በፊት*
ጨ5 *ጴጥሮስን ማለት ነው*

15፥2 *አጥብቃችሁ ብትይዙ፤* የዕብ 3፥14 ማብ ይመ። *ያመናችሁት በከንቱ ነው፤* በእምነቱ ጸንቶ የማይቆም ሰው ቀድሞውኑ እውነተኛ እምነት አልነበረውም ማለት ነው (የኋላ ኋላ እውነተኛ አማኝ እንዳልሆነ የታወቀውን የአስቆሮቱ ይሁዳን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ)።

*15፥3-5፤* እዚህ ላይ የክርስቶስን ሞትና ትንሣኤ የሚያረጋግጡ ሁለት ማስረጃዎች ቀርበዋል፤ (1) የብሉይ ኪዳን ምስክርነት (ለምሳሌ መዝ 16፥8-11፤ ኢሳ 53፥5-6:11)፤ (2) የዐይን ምስክሮች (ሐሥ 1፥ 21-22)። እዚህ ላይ ጌታ ኢየሱስ ከትንሣኤው በኋላ ስድስት ጊዜ መታየቱ ተዘርዝሯል። በወንጌላት ግን ከዚህም በላይ ይጠቀሳሉ።

15፥3 *እኔ የተቀበልሁትንና ከሁሉ በላይ የሆነውን ለእናንተ አስተላልፌአለሁ፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ ራሱን ከጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት ጋር ያዛምዳል። የትውፊቱ ምንጭ እርሱ አልነበረም፤ ከጌታም በቀጥታ አልተቀበለም። ትውፊቱን የተቀበለው ከሌሎች ክርስቲያኖች ነው። የተጠቀመባቸው ግሦች ትውፊትን መቀበልንና ማስተላለፍን የሚገልጹ መደበኛ ቃላት ናቸው (የ11፥23 ማብ ይመ)። ከዚህ በኋላ የሚያቀርበው የወንጌል መሪ ሐሳብ ነው፤ ይኸውም ክርስቶስ ስለ ኀጢአታችን መሞቱ (የሞተው ለራሱ ኀጢአት አይደለም፤ ዕብ 7፥27 ጋር ያነጻጽሩ)፣ መቀበሩ'ና (በእርግጥ መሞቱን የሚያሳይ ነው) ከሞት መነሣቱን የሚገልጽ ነው።

15፥4 *በሦስተኛው ቀን፤* ከማቴ 12፥40 ጋር ያነጻጽሩ። አይሁድ የአንድ ቀን ግማሽን ሙሉ ቀን ይቈጥሩ ነበር። ስለዚህ ሦስት ቀን ሲባል ዓርብ ከሰዓት በኋላን፣ ቅዳሜን ሙሉ ቀንና እሑድ ጧትን ያካትታል። ተመሳሳይ የጊዜ አቈጣጠር በዮሐ 20፥26 ይገኛል።

15፥5 *ለኬፋ ... ለዐሥራ ሁለቱ፤* ለጴጥሮስ የታየው እሑድ የፋሲካ ዕለት ሲሆን፣ ይህም በሉቃ 24፥34 ላይ ተጠቅሶአል፤ ለዐሥራ ሁለቱ የታየው እሑድ ምሽት ላይ ይመስላል (ሉቃ 24፥36-43፤ ዮሐ 20፥19-23 ይመ)። "ዐሥራ ሁለቱ" ሲባል የአስቆሮቱ ይሁዳ ከእነርሱ ጋር ባይሆንም፣ ለመጀመሪያዎቹ ሐዋርያት የተሰጠ መጠሪያ ነው (ይሁን እንጂ "ዐሥራ አንዱ ደቀ መዛሙርት"፣ "ዐሥራ አንዱ ሐዋርያት" ወይም "ዐሥራ አንዱ" በመባል በማቴ 28፥16፤ በማር 16፥14፤ በሉቃ 24፥9:33፤ በሐሥ 1፥26 ላይ የተጠቀሰውን ያስተውሏል)።

15፥6 *ከአምስት መቶ በላይ ... በአንድ ጊዜ፤* ቍጥራቸው ይህን ለሚያህል ሰዎች መታየቱ እዚህ ላይ የተነገረው የክርስቶስን ከሙታን መነሣት የተጠራጠሩትን የቆሮንቶስ ሰዎች እምነት ለማጠንከር ነው (ከቍ 12 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህ መታየት በማቴ 28፥10: 16-20 ላይ ከሙታን የተነሣው ጌታ ለዐሥራ አንዱና ምናልባትም ለብዙዎች ሰዎች የታየበት ጊዜ ሳይሆን አይቀርም። *አንዳንዶቹ ግን አንቀላፍተዋል፤* በዚያን ዘመን የአንድን ሰው መሞት የሚገልጽ የተለመደ አባባል ነው (ከሐሥ 7፥60 ጋር ያነጻጽሩ)።

15፥7 *ለያዕቆብ፤* ይህ ያዕቆብ የተጠቀሰው ከሐዋርያት በተጨማሪ በመሆኑ፣ የዘብዴዎስ ልጅ ወይም የእልፍዮስ ልጅ አይደለም (ማቴ 10፥2-3)። ይህኛው ያዕቆብ ከትንሣኤ በፊት በክርስቶስ ያላመነውና (ዮሐ 7፥5) የጌታ ወንድም (ገላ 1፥19) የተባለው ነው፤ እርሱም ከጊዜ በኋላ ከሐዋርያት ጋር በመቀላቀል (ሐሥ 1፥14)፣ በኢየሩሳሌም ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ትልቅ ስፍራ ነበረው (ሐሥ 15፥13)። ጌታ ለያዕቆብ የታየው መቼና የት እንደሆነ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በግልጽ አልተጠቀሰም። *ለሐዋርያት በሙሉ፤* ለምሳሌ ሐሥ 1፥6-11 ይመ።

15፥8 *ከሁሉም በኋላ፤* ሐሥ 9፥1-8 ይመ። ጌታ ለጳውሎስ የታየው፣ ከትንሣኤው በኋላ ብዙ ዓመት ቈይቶ (ምናልባት በ33 ዓ.ም. አካባቢ) ነበር። *እንደ ጭንጋፍ ለምቈጠር፤* ጳውሎስ ከመጀመሪያዎቹ ሐዋርያት አንዱ አልነበረም። እንደ ሌሎቹ ሐዋርያት ከጌታ ጋር አልኖረም። አጠራሩ እንደ ሌሎቹ ሐዋርያት አልነበረም፤ ባመነም ጊዜ ከቀድሞ ሕይወቱ የተነጠለው ድንገት ነው (ሐሥ 9፥3-6)።

15፥9 *የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን፤* ቤተ ክርስቲያን ሲያሳድድ፣ በእርግጥ ያሳደደው ክርስቶስን ነበር (ሐሥ 9፥4-5 ይመ)።

*15፥1-19፤* አንዳንድ የቆሮንቶስ ሰዎች የሙታን ትንሣኤ የለም ይሉ ነበር፤ ጳውሎስ ይህን የተሳሳተ አመለካከት ለመለወጥ በርካታ ማስረጃዎችን ያቀርባል። ሙታን የማይነሡ ከሆነ (1) "ክርስቶስ አልተነሣም ማለት ነዋ" (ቍ 13) (2) "ስብከታችን ዋጋ ቢስ ነው" (ቍ14)፤ (3) "እምነታችንም ከንቱ ነው" (ቍ14) (4) እግዚአብሔር ክርስቶስን ከሙታን አስነሥቶታል በማለታችን "ሐሰተኞች ... ምስክሮች" ሆነናል (ቍ15)፤ (5) "እምነታችሁ ከንቱ ነው" (ቍ17)፤ (6) "እስከ አሁን ድረስ ከነኀጢአታችሁ አላችሁ ማለት ነው" (ቍ17)፤ ደግሞም በኀጢአት ኵነኔ ሥር ናችሁ፤ (7) "በክርስቶስ ያንቀላፉት ጠፍተዋል ማለት ነው" (ቍ18)፤ (8) ስደትና መከራ የምንጋፈጠው ደግሞም "ክርስቶስን ተስፋ ያደረግነው ለዚህች ሕይወት ብቻ ከሆነ ... የምናሳዝን ነን" (ቍ19)።

15፥12 *ክርስቶስ ከሙታን እንደ ተነሣ፤* ክርስቶስ ከሙታን የተነሣው በሦስተኛው ቀን ነው፤ ይህም ታሪካዊ እውነታ ነው። ጳውሎስ ክርስቶስ በአካል ከሙታን እንደተነሣ የሚገልጸውን ግሥ በዚህ ክፍል ውስጥ ሰባት ጊዜ ተጠቅሞበታል (ቍ 4:12-14፡ 16-17፡ 20)።

# የሐዋርያው ጳውሎስ መልእክት
# ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች - አንደኛ

## መግቢያ

### የተሰሎንቄ መልእክቶች ዳራ

ወደ ተሰሎንቄ ከተላኩት መልእክታት ውስጥ ጳውሎስንና የሥራ ባልደረቦቹን የተዝዘብቸውንም ቦታዎች ከተሰሎንቄ መልእክታት ጋር በማዛመድ መመልከት ለምናደርገው ጥናት ጠቃሚ ነው። የተዝዘብቸው ቦታዎች የሚከተሉት ናቸው:-

(1) ጳውሎስና ሲላስ ከተሰሎንቄ ወደ ቤርያ ሸሹ (ሐሥ17፥10)፤ ጢሞቴዎስ ግን አልተጠቀሰም፤ ምክንያቱም በተሰሎንቄ ቀርቶ ሊሆን ይችላል፤ ወይም ወደ ፊልጵስዩስ ከተመለሰ በኋላ በቤርያ ከጳውሎስና ከሲላስ ጋር እንደ ገና ተገናኝቶ ይሆናል (ሐሥ17፥1)።

(2) ጳውሎስ በቤርያ ተከስቶ ከነበረው ስደት የተነሣ ሲላስንና ጢሞቴዎስን በቤርያ ትቶ ወደ አቴና ሸሸ (ሐሥ17:14)

(3) ጳውሎስ አቴና ሆኖ ሲላስና ጢሞቴዎስ ወደ እርሱ እንዲመጡ መልእክት ላከ (ሐሥ17፥15) እንዲሁም የ3፥1-2 ማብ ይመ)

(4) ጢሞቴዎስ በአቴና ጳውሎስን አገኘው፤ ከዚያም ጳውሎስ ጢሞቴዎስን፤ ወደ ተሰሎንቄ ላከው ። (3፥1-5 ይመ) በዚህ ስፍራ ሲላስ ስላልተጠቀሰ ምናልባት ጢሞቴዎስ ወደ ተሰሎንቄ ሲሄድ እርሱ ደግሞ ወደ ፊልጵስዩስ እንደተመለሰ ይገመታል።

(5) ጳውሎስ ወደ ቆሮንቶስ ሄደ (ሐሥ18፥1 ይመ)

(6) ሲላስና ጢሞቴዎስ ጳውሎስን ለማግኘት ወደ ቆሮንቶስ መጡ (3፥6፤ሐሥ18፥5 ይመ)

(7) ጳውሎስ 1ኛ ተሰሎንቄን ጽፎ ወደ ቤተ ክርስቲያን ላከ።

(8) ስድስት ወር ያህል ቈይቶ (51/52-44/45 ዓ.ም ) ስለ ቤተ ክርስቲያኒቱ በሰማው ሁኔታ ላይ ተመሥርቶ 2ኛውን የተሰሎንቄ መልእክት ጽፎአል።

### ጸሐፊው፣ መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ

ጳውሎስ ይህን መልእክት ቆሮንቶስ በነበረበት ወቅት እንደ ጻፈው ውስጣዊም ሆነ ውጭያዊ መረጃዎች ይመሰክራሉ (የ3፥1-2 ማብ ይመ)። በጥንት ቤተ ክርስቲያን የነበሩ ጸሐፊዎችም በዚህ ጉዳይ ላይ ይስማማሉ (ለምሳሌ ማርሲዮን 140 ዓ.ም )። ጳውሎስ የሚታወቅበት ባሕርይ በዚህ ደብዳቤ ውስጥ ተንጸባርቆአል (3፥1-2:8-11)፤ ከሐሥ15፥36፤ 2ቆሮ11፥28 ጋር ያነጻጽሩ)። በመልእክቱ ውስጥ የተጠቀሱት ታሪካዊ ሁኔታዎች በሐዋርያት ሥራና በሌሎች የጳውሎስ መልእክታት ስለ ጳውሎስ ሕይወት ከተጻፈው ታሪክ ጋር ይስማማሉ። (2፥14-16 ን ከሐሥ17፥5-10 ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም 3፥6 ን ሐሥ17፥16 ጋር ያነጻጽሩ)። በዚህ መረጃ መሠረት ጳውሎስ የ1ኛ ተሰሎንቄ ጸሐፊ መሆኑን የሚቃወሙ ሰዎች ጥቂት ናቸው። መልእክቱ እ.ኤ.አ በ51 ዓ.ም እንደ ተጻፈ ይገመታል፤ ለዚህም በግሪክ አገር ዴልፊ ከተባለ አካባቢ የተገኘው የጥንት ጽሑፍ አስተማማኝ ማስረጃ ነው፤ ይህም ጋሊዮ የተባለ የሮም ቆንሲል በተሾመበት በ51-52 ዓ.ም ጳውሎስም በቆሮንቶስ በነበረበት ጊዜ መሆኑ ነው። (ሐሥ18፥12-17 ይመ) የገላትያ መልእክት ከሁሉ አስቀድሞ እንደ ተጻፈ (48/41-49/42 ዓ.ም) ከሚሰጠው ግምት በስተቀር፣ ከጳውሎስ መልእክቶች ሁሉ በቅድሚያ የተጻፈው 1ኛ ተሰሎንቄ ነው።

### የተሰሎንቄ ከተማና ቤተ ክርስቲያን

የተሰሎንቄ ከተማ በቴርማይክ የባሕር ሰላጤ ራስጌ የምትገኝና ከፍተኛ እንቅስቃሴ ያለባት የወደብ ከተማ ነበረች። ተሰሎንቄ በታላቁ በኢግናቲያን መንገድ መገናኛ ላይ ስለምትገኝ የታወቀች የመገናኛና የንግድ ማዕከል ሆና ነበር። 200.000 ሕዝብ ይኖርባት ስለ ነበር በመቄዶኒያ ካሉት ከተሞች ሁሉ ታላቅዋ እርስዋ ናት። የክፍለ አገሯ ዋና ከተማም ነበረች። የተሰሎንቄ ቤተ ክርስቲያን ታሪካዊ ዳራ በሐሥ17፥1-9 ላይ ይገኛል፤ በዚህች ከተማ ጳውሎስ አገልግሎቱን የጀመረው በአይሁድ ምኵራብ ውስጥ ስለ ነበር በቤተ ክርስቲያኒቱ ውስጥ ጥቂት አይሁድ ይገኙ እንደ ነበረ መገመት አያዳግትም፤ ይሁን እንጂ በ1፥9-10፤ሐሥ17፥4 ላይ የቤተ ክርስቲያኒቱ አባላት በአብዛኛው ከአሕዛብ ወገን ወደ ጌታ የመጡ መሆናቸው ተጠቅሷል።

### ዐላማው

ጳውሎስ በተሰሎንቄ ከተማ ለጥቂት ጊዜ ከቈየ በኋላ በድንገት ከተማዋን ለቆ ወጣ (ሐሥ17፥5-10)፤ በዚህ ምክንያት ከአሕዛብ ወደ ጌታ የመጡትን አዳዲስ አማኞች በስደቱ ውስጥ የሚያጽናናቸው አልነበረም፣ ጳውሎስም ይህን መልእክት የጻፈበት ዐላማ በፈተና ውስጥ የነበሩትን አዳዲስ አማኞች ለማጽናናት ነበር (3፥3-5)። ይኸውም:- እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ እንዲኖሩ መመሪያ ለመስጠት (4፥1-8) ዕለታዊ ሥራቸውን እንዳያቋርጡ ለመምከር (4፥11-12)፤ ከክርስቶስ ዳግም ምጽአት በፊት ስለ ሚሞቱት አማኞች የወደ ፊት ሁኔታ (ተስፋ) ማረጋገጫ ለመስጠት ነው። (መሪ ሐሳቡን፤ የ4፥13:15 ማብ ይመ)።

**መሪ ሐሳቡ**

ደብዳቤው ለተለያየ ዐላማ የተጻፈ ቢሆንም ሁለቱም የተሰሎንቄ መልእክታት በመጨረሻው ዘመን በሚሆኑ ነገሮች ላይ ትኵረት ያደርጋሉ። የተሰሎንቄ መልእክታት በይበልጥ የሚናገሩት ስለትምህርተ ፍጻሜ ወይም ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት ነው። እያንዳንዱ የ1ኛ ተሰሎንቄ ምዕራፍ የሚደመደመው የክርስቶስን ዳግም ምጽአት በማመልከት ነው። ም4 ስለ ዳግም ምጽአት ትኵረት ይሰጣል (1፥9-10፤2፥19-20፤3፥13፤4፥13-18፤5፥23-24)። ስለዚህ የጌታ ምጽአት ጕዳይ በመልእክቱ ውስጥ ሰፊውን ቦታ የያዘ በመሆኑ መሪ ሐሳብ ተደርጎ ሊቈጠር ይችላል፤ ሁለቱም መልእክታት አብዛኛውን ጊዜ ጳውሎስ ስለ መጨረሻው ዘመን የጻፋአቸው ደብዳቤዎች ተብለው ይታወቃሉ።

**አስተዋፅኦ**

1. ስለ ተሰሎንቄ ሰዎች የቀረበ ምስጋና (ም1)
   ሀ. የምስጋና መንሥኤ (1፥1-4)
   ለ. የመንሥኤው እውነተኛ (1፥5-10)
2. ስለ ሐዋርያዊ አገልግሎቱና ከእነርሱ ስለ ተለየበት ምክንያት የተሰጠ መከላከያ (ም2-3)
   ሀ. ስለ ሐዋርያዊ አገልግሎቱ የቀረበ መከላከያ (2፥1-16)
   ለ. ወደ ተሰሎንቄ ስላለመምጣቱ የተሰጠ መግለጫ (2፥17-3፥10)
   ሐ. ጸሎት (3፥11-13)
3. ለተሰሎንቄ ሰዎች የተሰጠ ምክር (4፥1-5፥22)
   ሀ. ስለ ግላዊ ሕይወት (4፥1-12)
   ለ. ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት (4፥13-5፥11)
   ሐ. ስለ ቤተ ክርስቲያን ሕይወት (5፥12-22)
4. ማጠቃለያ ጸሎት፣ ሰላምታና ቡራኬ (5፥23-28)

**1** ከጳውሎስ፣ ከሲላስና[ሀ] ከጢሞቴዎስ፤ የእግዚአብሔር አብና የጌታ የኢየሱስ ክርስቶስ ለሆኑት ለተሰሎንቄ ሰዎች ቤተ ክርስቲያን፤

ከእግዚአብሔር ከአባታችን ከጌታም ከኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋና ሰላም ለእናንተ ይሁን[ለ]።

## ስለ ተሰሎንቄ ሰዎች እምነት የቀረበ ምስጋና

[2]በጸሎታችን እያስታወስናችሁ ሁልጊዜ እግዚአብሔርን ስለ ሁላችሁ እናመሰግናለን። [3]ከእምነት የሆነውን ሥራችሁን፣ ከፍቅር የመነጨውን ድካማችሁንና በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ባላችሁ ተስፋ የተገኘውን ጽናታችሁን በአምላካችንና በአባታችን ፊት ዘወትር እናስባለን።

[4]እግዚአብሔር የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ፤ እርሱ እንደ መረጣችሁ እናውቃለን፤ [5]ምክንያቱም ወንጌላችን ወደ እናንተ የመጣው በኀይልና በመንፈስ ቅዱስ በብዙም መረዳት እንጂ በቃል ብቻ አይደለም። ደግሞ ስለ እናንተ ስንል በመካከላችሁ እንዴት እንደኖርን ታውቃላችሁ። [6]እናንተ እኛንና ጌታን መስላችኋል፤ ምንም እንኳ ብርቱ መከራ ቢደርስባችሁም ቃሉን በመንፈስ ቅዱስ ደስታ ተቀብላችኋል። [7]ከዚህም የተነሣ በመቄዶንያና በአካይያ ለሚገኙ ምእመናን መልካም ምሳሌ ሆናችኋል። [8]የጌታ ቃል ከእናንተ ወጥቶ በመቄዶንያና በአካይያ መሰማቱ ብቻ ሳይሆን በእግዚአብሔር ያላችሁ እምነት በሁሉ ቦታ ታውቆአል፤ ስለዚህ እኛ በዚህ ጕዳይ ላይ ምንም መናገር አያስፈልገንም፤ [9]በእንዴት ያለ አቀባበል እንደ ተቀበላችሁንና ሕያውና እውነተኛ የሆነውን እግዚአብሔርን ለማገልገል ከጣዖታት ወደ እግዚአብሔር እንዴት እንደ ተመለሳችሁ እነርሱ ራሳቸው ይናገራሉ፤ [10]ደግሞም ከሙታን ያስነሣውንና ከሰማይ የሚመጣውን ልጁን፣ ከሚመጣውም ቍጣ የሚያድነንን ኢየሱስን እንዴት እንደምትጠባበቁ ይናገራሉ።

## የጳውሎስ አገልግሎት በተሰሎንቄ

**2** ወንድሞች ሆይ፤ ወደ እናንተ የመጣነው ለከንቱ እንዳልሆነ እናንተ ራሳችሁ ታውቃላችሁ።

*ሀ1 ግሪኩ ሲሉያኖስ ይላል*

*ለ1 አንዳንድ ቅጂዎች ከእግዚአብሔር ከአባታችን ከጌታም ከኢየሱስ ክርስቶስ የሚለው የላቸውም*

1፥1 ሐሥ15፥22፤ 16፥1፤17፥1፤ ሮሜ1፥7፤2ተሰ1፥1
1፥2 ሮሜ1፥8፡10፤ ኤፌ5፥20
1፥3 ሮሜ8፥25፤ 1ቆሮ13፥13፤ገላ5፥6፤ ፊል4፥20፤1ተሰ3፥6፤ 2ተሰ1፥3፡11፤ያዕ2፥14-26
1፥4 ቈላ3፥12፤ 2ተሰ2፥13
1፥5 ሮሜ1፥16፤ 15፥13፤2ቆሮ2፥12፤ 1ተሰ2፥10፤ 2ተሰ2፥14
1፥6 ሐሥ13፥52፤ 17፥5-10፤ 1ቆሮ 4፥16፤ 2ቆሮ6፥10
1፥7 ሐሥ16፥9፤ 18፥12፤1ጢሞ4፥12
1፥8 ሮሜ1፥8፤ 2ተሰ3፥1
1፥9 ማቴ16፥16፤ ሐ14፥15፤1ቆሮ12፥2፤ገላ4፥8
1፥10 ሐሥ2፥24፤ ሮሜ1፥18፤1ቆሮ1፥7
2፥1 1ተሰ1፥5፡9፤ 2ተሰ1፥10

1፥1 *ከጳውሎስ፤* የሐሥ9፥1፤13፥9፤ ፊል3፥4-14 ማብ ይመ። *ከሲላስ፤* የሐሥ15፥22 ማብ ይመ። በሁለተኛው የጳውሎስ የወንጌል ጕዞ ብዙ ጊዜ አብሮት ተጕዞአል (ሐሥ 15፥22-18፥5)። *ከጢሞቴዎስ፤* ከ1ኛ ጢሞቴዎስ መግቢያ፣ "ተደራሲው" የሚለውን ይመ፤ ከሲላስ ጋር በመሆን የተሰሎንቄን ቤተ ክርስቲያን ለመመሥረት ጳውሎስን ረድተውታል (ሐሥ17፥1-14)። *ከእግዚአብሔር...ከጌታ፤* ክርስቲያኖች ከአብና ከወልድ ጋር ያላቸውን ጠንካራ ግንኙነትንና ሕያው ኅብረትን ያመለክታል (ዮሐ14፥23፤ 17፥21)። የግሪኩ ሰዋስው አብና ወልድ የተለያየ አካል እንዳላቸው ያሳያል። በአብና በወልድ መካከል ያለው ግንኙነት የሥላሴን ግንኙነት ያመለክታል (3፥11፤2ተሰ1፥2፡8፡12፤2፥16፤3፥5)። *ጸጋና ሰላም፤* የዮና 4፥2፤ ዮሐ14፥27፤20፥19፤ገላ1፥3 ኤፌ1፥2 ማብ ይመ።

1፥2 *እናመሰግናለን፤* የፊል1፥3-4 ማብ ይመ።

*1፥3፤* በአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ እምነት፣ ተስፋና ፍቅር ብዙ ጊዜ በአንድነት ተጠቅሰው ይገኛሉ (5፥8፤ሮሜ5፥2-5፤1ቆሮ 13፥13፤ገላ5፥5-6፤ቈላ1፥4-5፤ዕብ6፥10-12፤10፥22-24፤1ጴጥ1፥3-8፡ 21-22)። *ከእምነት የሆነውን ሥራችሁን፤* እምነት በተግባር ይገለጣል (ሮሜ1፥5፤ 16፥26፤ ገላ5፥6 ፤2ተሰ1፥11፤ያዕ2፥14-26 ይመ)። *ተስፋ፤ መሠረት የሌለው የምኞት ሐሳብ* ሳይሆን በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስና በዳግም ምጽአቱ ላይ የተመሠረተ እምነት ነው (ቍ 10)። ዕብ 6፥18-20 እና የቈላ1፥5 ማብ ይመ፡

1፥4 *የተወደዳችሁ...መረጣችሁ፤* ሁለቱም ቃላት የእግዚአብሔርን ፍቅር ይገልጻሉ (ቈላ3፥12፤2ተሰ2፥13፤ የኤፌ1፥4 ማብ ይመ)። *ወንድሞች፤* ከክርስቶስ ጋር ባለ ኅብረት የሚመጣ አንድነት ነው። ለተሰሎንቄ ክርስቲያኖች በተጻፉት ሁለት መልእክቶች ውስጥ ይህ ቃል ሃያ ስምንት ጊዜ ያህል ተጠቅሶአል። *እናውቃለን፤* ጳውሎስ መመረጣቸውን በሚመለከት ጽኑ እምነት እንዲኖረው ያደረገው ምክንያት ከቍ 5-10 ላይ ተጠቅሶአል።

1፥5 *ወንጌላችን፤* በጳውሎስ፣ በሲላስና በጢሞቴዎስ የተሰበከውንና እነርሱም በእምነት የተቀበሉትን ወንጌል ያመለክታል። ወንጌል ከሁሉ አስቀድሞ እግዚአብሔር አብ ስለ ጀመረው የእርሱ ነው (2፥8)፤ ደግሞም ለኀጢአታችን ሥርየት በክርስቶስ ሞት ላይ የተመሰረተ ስለ ሆነ የክርስቶስም ነው (3፥2)። *ኀይል፤* ከመንፈሳዊ ባርነት ነጻ የሚያወጣ ኀይል ነው፤ ይኸውም የመንፈስ ቅዱስ ኀይል ነው (ሮሜ15፥13፡18-19፤1ቆሮ2፥4-5 ይመ)፤ ደግሞም ይህ ኀይል በወንጌል ውስጥ አለ (ሮሜ1፥16 ይመ)። *በብዙም መረዳት፤* በሰባኪዎቹም ሆነ በተሰሎንቄ ክርስቲያኖች ዘንድ የነበረው ይህ መረዳት ከመንፈስ ቅዱስ ነው።

1፥6 *መስላችኋል፤* ክርስቲያን መከተል የሚገባው የመልካም ምሳሌነት ደረጃዎች፡- (1) የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች በይሁዳ ያሉትን አብያተ ክርስቲያናት ምሳሌነት እንደተከተሉ (2፥14)፣ በመቄዶንያና በአካይያ ያሉ አማኞች የተሰሎንቄን ክርስቲያኖች ምሳሌነት ተከትለዋል (ቍ7)፤ (2) የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች የጳውሎስን ምሳሌነት እንደ ተከተሉና (1ቆሮ 4፥6፤ 11፥1) አማኞች ሁሉ የመሪዎቻቸውን ምሳሌነት እንደሚከተሉ የተሰሎንቄ ክርስቲያኖችም የጳውሎስን ምሳሌነት ተከትለዋል (2ተሰ3፥7፡9፤ 1ጢሞ 4፥12፤ቲቶ2፥7፤1ጴጥ5፥3)፤ (3) ጳውሎስ የክርስቶስን ምሳሌነት እንደ ተከተለ የተሰሎንቄም ክርስቲያኖች የክርስቶስን ምሳሌነት ተከትለዋል (ቍ6)፤ (4) ሁሉም እግዚአብሔርን ለመምሰል ይሆን አደረጉ (ኤፌ5፥1)። *ብርቱ መከራ፤* በሐሥ17፥5-14 እንደ ተዘገበው ነው (1ተሰ2፥14 ይመ)።

1፥7 *በመቄዶንያና በአካይያ፤* በዚያን ዘመን ግሪክ የተከፋፈለችባቸው ሁለት የሮማ ክፍላተ አገራት ነበሩ (ሐሥ19፥21፤ ሮሜ15፥26 ይመ)።

1፥8 *በሁሉ ቦታ፤* በጎበኙበትና በሚያውቁት ስፍራ ሁሉ ማለት ነው (ሮሜ1፥8፤ 1ቆሮ1፥2፤ 2ቆሮ2፥14፤ 1ጢሞ2፥8)። የምሥራቹ በፍጥነት የተሠራጨበት ምክንያት የተሰሎንቄ ከተማ በዋናው የኢግኒሽያን መንገድ ላይ በመሆንዋ ከፍተኛ የንግድ እንቅስቃሴ የሚካሄድበት ወደብና የሮማ ግዛት የሆነችው የመቄዶንያ ዋና ከተማ ስለ ነበረች ነው።

*1፥9-10፤* እውነተኛ ለውጥን የሚያመለክቱ ሦስት ምልክቶች፡- (1) ከጣዖት አምልኮ መመለስ፤ (2) እግዚአብሔርን ማገልገልና (3) የክርስቶስን ዳግም ምጽአት መጠባበቅ ናቸው። ጳውሎስ ለተሰሎንቄ ሰዎች በጻፋቸው ሁለት አጫጭር መልእክቶቹ በብዛት የሚናገረው ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት ነው (ቍ10፤ 2፥19፤ 3፥13፤ 4፥13-5፥4፤ 2ተሰ1፥7-10፤ 2፥1-12)።

1፥10 *ኢየሱስ፤* "የሹዋ" ከሚለው የዕብራይስጥ ቃል የተወሰደ ሲሆን ትርጕሙም፣ "እግዚአብሔር ያድናል" ማለት ነው። *ቍጣ፤* አንዳንዶች ቃሉ የመጨረሻውን ፍርድ እንደሚያመለክት አድርገው ሲያስቡ (የሮሜ 1፥18 ማብ ይመ)፣ ሌሎች ግን ወደ ፊት ያለውን ታላቁን መከራ ያመለክታል ይላሉ።

*2፥1-12፤* ለአገልጋይ የሚሆን "መመሪያ" ነው ይኸውም፡- (1) የእርሱ መልእክት የእግዚአብሔር መልካም ዜና ነው ("ወንጌል")፤ (2) የተነሣበትም ዐላማ ክፉት ላይ የተመሠረተ አይደለም (ቍ3)፤ ሰዎችን ደስ ለማሰኘት (ቍ4) በሥሥት (ቍ5) ወይም ከሰዎች ምስጋናን ለማግኘት ሳይሆን (ቍ6) እግዚአብሔርን ደስ ለማሰኘት ነው (ቍ4) (3) ተግባሩ በማታለል (ቍ3)፣ በሽንገላ (ቍ5) ወይም በስውር ሳይሆን (ቍ5)፣ በሙሉ ልብ (ቍ2)፣ በየዋህነት (ቍ7)፣ በፍቅር (ቍ8፡11)፣ በድካም እና(ቍ9) በቅድስና ነው (ቍ10)።

2፥1 *ታውቃላችሁ፤* አጥቢያ ቤተ ክርስቲያኒቱ በጳውሎስ ላይ ተቃዋሚዎች የተሰነዘሩት የእምነት ማጉደል ክስ መቃወም ችላለች (ቍ3)።

[2]እንደምታውቁት ከዚህ ቀደም በፊልጵስዩስ መከራ ተቀብለን ተንገላታን፤ ነገር ግን ብርቱ ተቃውሞ ቢደርስብንም እንኳ የእግዚአብሔርን ወንጌል ለእናንተ እንደምናበሥር በአምላካችን ድፍረት አገኘን:: [3]የምናቀርበው ልመና ከስሕተት ወይም ከክፉ ዐላማ ወይም እናንተን ለማታለል ከመፈለግ የመነጨ አይደለም:: [4]ነገር ግን ወንጌልን በዐደራ ለመቀበል እግዚአብሔር ብቁ አድርጎ እንደ ቈጠራቸው ሰዎች ሆነን እንናገራለን:: ይህንንም የምናደርገው ልባችንን የሚመረምረውን እግዚአብሔርን እንጂ ሰዎችን ደስ ለማሰኘት ብለን አይደለም:: [5]የሽንገላ ቃል ከቶ እንዳልተናገርን ወይም ሥሥትን ለመሸፈን ብለን አስመሳዮች እንዳልሆንን ታውቃላችሁ፤ ለዚህም እግዚአብሔር ምስክራችን ነው:: [6]ከእናንተም ሆነ ከሌሎች ከማንም፣ ከሰው የሚገኝ ክብር አልፈለግንም:: የክርስቶስ ሐዋርያት እንደ መሆናችን መጠን ሸክም በሆንባችሁ ነበር፤ [7]ነገር ግን እናት ልጆቿን እንደምትንከባከብ እኛም በመካከላችሁ በየዋህነት ተመላለስን::

[8]የእግዚአብሔርን ወንጌል ብቻ ሳይሆን ሕይወታችንን ጭምር ልናካፍላችሁ ደስ እስኪለን ድረስ ወደድናችሁ፤ ምክንያቱም እናንተ በእኛ ዘንድ ተወዳጆች ነበራችሁ:: [9]ወንድሞች ሆይ፤ ጥረታችንንና ድካማችንን ታስታውሳላችሁ፤ በማንም ላይ ሸክም እንዳንሆን ሌሊትና ቀን እየሠራን ወንጌል ሰበክንላችሁ::

[10]በእናንተ በምታምኑት መካከል ሳለን እንዴት በቅድስና፣ በጽድቅ እንዲሁም ያለነቀፋ ሆነን እንደኖርን እናንተም እግዚአብሔርም ምስክሮች ናችሁ:: [11]አባት ለገዛ ልጆቹ እንደሚሆን እኛም ለእያንዳንዳችሁ የቱን ያህል እንደ ሆንን ታውቃላችሁ፤ [12]ወደ መንግሥቱና ወደ ክብሩ ለጠራችሁ ለእግዚአብሔር እንደሚገባ ትኖሩ ዘንድ አበረታታናችሁ፤ አጽናናችሁ፤ አጥብቀን ለመንናችሁ::

[13]ከእኛ የሰማችሁትን የእግዚአብሔርን ቃል በተቀበላችሁ ጊዜ፣ በእናንተ በምታምኑት ዘንድ በእርግጥ እንደሚሠራ እንደ እግዚአብሔር ቃል እንጂ እንደ ሰው ቃል አድርጋችሁ ስላልተ ቀበላችሁት እግዚአብሔርን ያለ ማቋረጥ እና መሰግናለን:: [14]ወንድሞች ሆይ፤ በክርስቶስ ኢየሱስ ያሉትን በይሁዳ የሚገኙትን የእግዚአብሔርን አብያተ ክርስቲያናት መስላችኋል፤ እነዚያ ከአይሁድ መከራ እንደ ተቀበሉ፣ እናንተም ከገዛ ወገኖቻችሁ መከራን ተቀብ ላችኋል:: [15]እነርሱ ጌታ ኢየሱስንና ነቢያትን ገደሉ፤ እኛንም አሳደዱን፤ እግዚአብሔ ርንም ደስ አላሰኙትም፤ የሰውም ሁሉ ፀር ሆኑ፤ [16]ይኸውም ይድኑ ዘንድ ለአሕዛብ እን ዳንናገር ለመከልከል ነው፤ በዚህ ሁኔታ ኀጢአታቸውን ሁልጊዜ በራሳቸው ላይ እስከ መጨረሻው እያከማቹ ይሄዳሉ:: ቍጣውም በእነርሱ ላይ ያለ ልክ መጥቶአል*::

## ጳውሎስ የተሰሎንቄን ሰዎች ለማየት የነበረው ናፍቆት

[17]ነገር ግን ወንድሞች ሆይ፤ እኛ በልባችን ሳይሆን በአካል ለጥቂት ጊዜ ከእናንተ ብንለይም፣ ለእናንተ ካለን ታላቅ ናፍቆት የተነሣ ፊታችሁን ለማየት ብርቱ ጥረት አደረግን:: [18]ወደ እናንተ ለመምጣት ፈልገን ነበር፤ በተለይም እኔ ጳውሎስ ብዙ ጊዜ ሞክሬ ነበር፤ ነገር ግን ሰይጣን አዘገየኝ::

*16 ወይም በሙላት መጥቶአል

2፥2 ሐሥ14፥19፤ 16፥12:22፤17፥1-9፤ፊል1፥30
2፥3 2ቆሮ2፥17፤ 4፥2
2፥4 ሮሜ፥29፤ ገላ2፥7፤1ጢሞ1፥11፤ ራእ2፥23
2፥5 ቍ10፤ ሐሥ20፥33፤ ሮሜ1፥9
2፥6 ዮሐ5፥41:44፤ 1ቆሮ9፥1:2፤ 2ቆሮ11፥7-11
2፥7 ቍ11
2፥8 ሮሜ1፥1፤ 2ቆሮ12፥15፤ 1ዮሐ3፥16
2፥9 ሐሥ18፥3፤ 2ቆሮ11፥9፤2ተሰ3፥8
2፥10 ቍ5፤ ሮሜ1፥9፤2ቆሮ1፥12፤ 1ተሰ1፥5
2፥11 ቍ7፤1ቆሮ 4፥14፤ ገላ4፥19፤ 1ጢሞ1፥2፤ፊሞ10፤ 1ዮሐ2፥1
2፥12 ሮሜ8፥28፤ ኤፌ4፥1
2፥13 ሮሜ1፥8፤ 1ተሰ1፥2፤ዕብ4፥12
2፥14 ሐሥ17፥5፤ ገላ1፥22፤1ተሰ1፥6፤2ተሰ1፥4
2፥15 ማቴ5፥12፤ ሉቃ24፥20፤ ሐሥ2፥23
2፥16 ማቴ23፥32፤ ሐሥ13፥45:50፤ 17፥5፤20፥3፤ 21፥27፤24፥9
2፥17 1ቆሮ5፥3፤ ቈላ2፥5፤1ተሰ3፥10
2፥18 ማቴ4፥10፤ ሮሜ1፥13፤15፥22

2፥2 *ተንገላታን፤* ጳውሎስ በፊልጵስዩስ ከተማ በደረሰበት መንገላታት ክፉኛ ተጐድቶአል (ሐሥ16፥19-40)::

2፥3 *ለማታለል፤* በግሪኩ ቋንቋ ይህ ቃል ዓሣን ለማጥመድ በመንጠቆ ላይ የሚደረገውን ምግብ ያመለክታል፤ በኋላ ግን ለጥቅም ሲባል የሚደረገውን ማንኛውንም ዐይነት ተንኰል ለማሳየት ጥቅም ላይ መዋል ጀመረ::

2፥4 *ልባችንን፤* ስሜታችንን ብቻ ሳይሆን አስተሳሰባችንንና ፈቃዳችንን ያመለክታል::

2፥5 *ሥሥትን ለመሸፈን፤* የጳውሎስ ዐላማ የግል ጥቅም ማግኘት አልነበረም::

2፥6 *ሸክም፤* ሐዋርያት ከቤተ ክርስቲያን ድጋፍ ሊደረግላቸው ይገባል (1ቆሮ9፥13-14፤2ቆሮ11፥7-11):: ጳውሎስ መብቱን መጠቀም የሚችል ሰው ቢሆንም እንኳ ሁልጊዜ የመብቱ ተጠቃሚ ሰው አልነበረም::

2፥7 *እናት ልጆዋን እንደምትንከባከብ፤* ጳውሎስና ረዳቶቹ፣ የወንጌል መልእክተኞች ወይም መጋቢዎች ወንጌልን ሲሰብኩ ሊኖራቸው ስለሚገባቸው መንፈሳዊነት መልካም አርአያ ትተው አልፈዋል፤ ይህ ትህትናና እንክብካቤ በመከራ ጊዜ ለመመገብ፣ ለመጠበቅና የአዳዲሶችን መንፈሳዊ ፍላጎት ለሟሟላት በከፈሉት መሥዋዕትነት ታይቶአል::

2፥9 *ጥረታችንንና ድካማችንን፤* ግሪኮች በእጅ የሚሠራን ሥራ አይወዱም፤ እንዲህ ዐይነቱ ሥራ ለባሪያዎች ብቻ የሚሆን ነው ብለው ያስባሉ:: ጳውሎስ ግን ወንጌልን ለማሠራጨት የሚረዳን ማንኛውንም ዐይነት ሥራ የሚንቅ ሰው አልነበረም፤ ያለ አግባብ በሌሎች ላይ ጥገኛ መሆንንም አይፈልግም ነበር::

2፥10፤ *እንዴት በቅድስና፤* የክርስቶስ ኢየሱስ ደም ከኀጢአት እስራትና ኀይል ነጻ ለማውጣት ብቃት የለውም የሚለውን የሐሰት ትምህርት ጳውሎስ አይቀበለውም፤ ይህንንም በተሰሎንቄ ክርስቲያኖች መካከል በቅድስና፣ በጽድቅና ያለ ነቀፋ በመኖር እንዳሳየ ይናገራል::

2፥12 *መንግሥቱ፤* ይህ የኢየሱስ ክርስቶስ ትምህርት ዋና ሐሳብ ነው:: ጳውሎስ ይህን ቃል ብዙ ጊዜ አልተጠቀመም፤ ነገር ግን የሰበከውን ስብከት ለማጠቃለል ሲል ብቻ አንዴ ተጠቅሞበታል (ሐሥ20፥25):: *ለጠራችሁ፤* የ1፥4 ማብ ይመ:: *ለእግዚአብሔር እንደሚገባ ትኖሩ ዘንድ፤* ኤፌ4፥1 ይመ::

2፥13 *እንደ ሰው ቃል...አድርጋችሁ፤* ከዘመኑ ሰዎች ዕውቀት ጋር ያልተደባለቀ ማለት ነው::

2፥14 *አይሁድ፤* ምንም እንኳ ጳውሎስ ለገዛ ወገኖቹ ድነት ትልቅ ናፍቆ ያለውና የሚገደው ሰው ቢሆንም እንኳ (ሮሜ9፥1-3፤10፥1 ይመ) ቤተ ክርስቲያንን የሚያሳድዱትን አይሁድ መገሠጹን ግን አላቋረጠም:: *እናንተም ከገዛ ወገኖቻችሁ መከራን ተቀብላችኋል፤* ጳውሎስ መጀመሪያ ተሰሎንቄን በጎበኘበት ጊዜ በአይሁድ የተቀነባበረ ስደት ከአሕዛብ ደርሶበታል (ሐሥ 17፥5-9)::

2፥15 *ነቢያት፤* በብሉይ ኪዳን ዘመን እስራኤላውያን ነቢያታቸውን ያሳድዱ ነበር (ሐሥ7፥52 ጋር ያነጻጽሩ)::

2፥16 *ቍጣው...መጥቶአል፤* በዘመን ፍጻሜ የሚሆነውን የእግዚአሔርን ቍጣ ያመለክታል፤ ይህም ኀጢአተኛ በሆነው የሰው ዘር ላይ የሚደርሰውን የእግዚአብሔርን ቍጣ ያሳያል (1፥10 ይመ):: ይህ የተነገረው በአሁን ጊዜ እንደ ሆን ተደርጐ ነው፤ ምክንያቱም በአይሁድ ላይ ይህ ቍጣ በከፊል ስለ ተፈጸመ ወይም መፈጸሙ ስለማይቀር ነው:: ጳውሎስም ወንጌልን የሚቃወሙትን አይሁድን ይቃወማል (ቍ14-16)፤ ደግሞም የእግዚአብሔር ቍጣ በእነርሱ ላይ እንደ ሆን ይናገራል::

2፥17 *ብንለይም፤* በቁሙ "ወላጅ የሌለው" ማለት ነው፤ ጳውሎስ ራሱን እንደ እናት (ቍ7)፣ እንደ አባት (ቍ 11)፣ እዚህ ቦታ ደግሞ ወላጅ እንደ ሌለው አድርጎ ያቀርባል::

19ጌታችን ኢየሱስ ሲመጣ በእርሱ ፊት ተስፋችን ወይም ደስታችን ወይም አክሊላችን ማን ነው? እናንተ አይደላችሁምን? 20በእርግጥ ክብራችንም ደስታችንም ናችሁ።

**3** ስለዚህ መታገሥ ስላልቻልን በጊዜ በአቴና ብቻችንን መቅረት መልካም መስሎ ታየን። 2በእምነታችሁ እንዲያጸናችሁና እንዲያበረታችሁ ወንድማችንንና በክርስቶስ ወንጌል ሥራ ከእኛ ጋር የእግዚአብሔር አገልጋይ[m] የሆነውን ጢሞቴዎስን ልከንላችኋል፤ 3ይኸውም በዚህ ፈተና ማንም እንዳይናወጥ ነው። እኛም ለዚህ ነገር እንደተመደብን እናንተ ራሳችሁ ታውቃላችሁ። 4በእርግጥ ከእናንተ ጋር በነበረንበት ጊዜ መከራ እንደሚደርስብን በየጊዜው እንነግራችሁ ነበር፤ እንደምታውቁትም እንዲሁ ደግሞ ሆኖአል። 5ስለዚህ ምንም መታገሥ ባልቻልሁ ጊዜ ስለ እምነታችሁ ለማወቅ ላክሁ፤ ይህንንም ያደረግሁት ምናልባት ፈታኙ ፈትኖአችሁ ድካማችን ሁሉ ከንቱ ሆኖአል ብዬ ስለ ፈራሁ ነው።

### ጢሞቴዎስ ይዞት የመጣው የምሥራች

6አሁን ግን ጢሞቴዎስ ከእናንተ ዘንድ ወደ እኛ መጥቶ ስለ እምነታችሁና ስለ ፍቅራችሁ መልካም ዜና አሰምቶናል። ደግሞም እኛን ሁልጊዜ በመልካም እንደምታስታውሱንና እኛ እናንተን ለማየት የምንናፍቃችሁን ያህል እናንተም እኛን ለማየት እንደምትናፍቁ ነግሮናል። 7ስለዚህ ወንድሞች ሆይ፤ በጭንቀታችንና በመከራችን ሁሉ በእምነታችሁ ምክንያት በእናንተ ተጽናናን። 8በጌታ ጸንታችሁ ስለ ቆማችሁ በእርግጥ አሁን በሕይወት እንኖራለን። 9በእናንተ ምክንያት በአምላካችን ፊት ስላገኘነው ደስታ ሁሉ ስለእግዚአብሔር ምን ያህል ምስጋና ልናቀርብ እንችላለን? 10እንደገና ልናያችሁና በእምነታችሁ የጐደለውን ለማሟላት ሌሊትና ቀን እጅግ ተግተን እንጸልያለን።

11አሁንም ራሱ አምላካችንና አባታችን፣ ጌታችንም ኢየሱስ ክርስቶስ ወደ እናንተ እንድንመጣ መንገዳችንን ያቅናልን። 12እኛ ለእናንተ ፍቅር እንዳለን ሁሉ እርስ በርስ ያላችሁን ፍቅርና ለሌሎችም ያላችሁን ፍቅር ጌታ ያብዛላችሁ፤ ያትረፍርፍላችሁም። 13ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከቅዱሳኑ ሁሉ ጋር በሚመጣበት ጊዜ በአምላካችንና በአባታችን ፊት ነቀፋ የሌለባችሁና ቅዱሳን ሆናችሁ እንድትገኙ ልባችሁን ያጽና።

### እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ አኗኗር

**4** በቀረውስ ወንድሞች ሆይ፤ እግዚአብሔርን ደስ ለማሰኘት እንዴት መኖር እንደሚገባችሁ

2፥19 ኢሳ62፥3፤ ማቴ16፥27፤ሉቃ17፥30፤1ቆሮ1፥7፤4፥5፤2ቆሮ1፥14፤ፊል4፥1፤ 1ተሰ3፥13፤2ተሰ1፥8-10፤1ጴጥ1፥7፤ 1ዮሐ2፥28፤ራእ1፥7
2፥20 2ቆሮ1፥14
3፥1 ቁ.5፤ ሐሥ17፥15
3፥2 ሐሥ16፥1፤ 1ቆሮ3፥9፤2ቆሮ2፥12
3፥3 ማር4፥17፤ ዮሐ16፥33፤ሐሥ9፥16፤ 14፥22፤ሮሜ 5፥3፤2ቆሮ1፥4፤ 4፥17፤ 2ጢሞ3፥12
3፥4 1ተሰ2፥14
3፥5 ቁ.1፡2፤ ማቴ4፥3፤ገላ2፥2፤ ፊል2፥16
3፥6 ሐሥ16፥1፤ 18፥5፤1ተሰ1፥3፡2፥17፡18
3፥8 1ቆሮ16፥13
3፥9 1ተሰ1፥2፤ 2፥19፡20
3፥10 1ተሰ2፥17፤ 2ጢሞ1፥3
3፥11 ቁ.13፤ ፊል4፥20
3፥12 ፊል1፥9፤1ተሰ4፥9፡10፤2ተሰ1፥3
3፥13 ቁ.11፤ መዝ15፥2፤ማቴ25፥31፤1ቆሮ1፥8፤ ፊል2፥15፤ 4፥20፤ 2ተሰ1፥7፤1ጢሞ6፥14፤ 2ጴጥ3፥14
4፥1 2ቆሮ5፥9፤ 13፥11፤ኤፌ4፥1፤2ተሰ3፥1

[m]2 አንዳንድ ቅጆዎች *ወንድማችንንና...ከእግዚአብሔር ጋር አብሮ የሚሰራ* ሲሉ ሌሎች ደግሞ *ወንድማችንንና...የእግዚአብሔር አገልጋይ* ይላሉ።

2፥19 ***አክሊላችን፤*** የንግሥና አክሊል ሳይሆን በበዓል ጊዜ ለክብር እንደሚሰጠው የአበባ ጉንጉን ወይም በግሪካውያን የስፖርት ውድድር ጊዜ እንደሚሰጠው ሽልማት ዐይነት ነው።

2፥20 ***ክብራችንም ደስታችንም ናችሁ፤*** ይህ አሁንም ሆነ (ከፊል4፥1 ጋር ያነጻጽሩ) በክርስቶስ ዳግም ምጽአት እውነት ነው።

*3፥1-2፤* ጳውሎስ በመጀመሪያ ብቻውን ወደ አቴና ሄደ፤ ከዚያም ቤሪያ ወደ ነበሩት ወደ ሲላስና ጢሞቴዎስ መልእክት ላከ (ሐሥ17፥14-15)። ነገር ግን ሲላስ እንደ ታዘዘው ከጢሞቴዎስ ጋር ወደ አቴና መምጣቱ ግልጽ አይደለም (ሐሥ17፥15)፤ ይሁን እንጂ ከተሰሎንቄ ጢሞቴዎስ ቆሮንቶስ ወደ ነበረው ወደ ጳውሎስ በመጣ ጊዜ ሲላስ ከእርሱ ጋር መጥቶአል (ሐሥ18፥5)። ከዚህ መጽሐፍ መግቢያ፣ "የተሰሎንቄ መልእክታት ታሪካዊ ዳራ" የሚለውን ይመ።

3፥2 ***እንዲያበረታችሁ፤*** በጥንታዊው ግሪክ ሥነ ጽሑፍ ቃሉ የሚያመለክተው ሕንጻን ለማጠናከር የሚሠራውን ድጋፍ ነው። እዚህ በታ እንደተጠቀሰው በአዲስ ኪዳንም በሥዕላዊ መግለጫነት ቀርቦአል። ***የክርስቶስ ወንጌል፤*** የ1፥5፤ ማር1፥1 ማብ ይመ። ***ከእኛ ጋር የእግዚአብሔር አገልጋይ፤*** ክርስቲያናዊ አገልግሎት ምን ያህል ክቡር እንደ ሆነ የሚያመለክት ነው (1ቆሮ 3፥9 ይመ)።

3፥3 ***ፈተና፤*** በተሰሎንቄ ክርስቲያኖች ላይ የደረሰውን ተቃውሞና ስደት ያመለክታል። ክርስቲያኖች ችግር ወይም መከራ ሊያጋጥማቸው እንደሚችል ማወቅ ይገባቸዋል (ማር4፥17፤ዮሐ16፥33፤ሐሥ14፥22፤2ጢሞ3፥12፤1ጴጥ4፥12 ይመ)። መከራ የሚደርስብን የእግዚአብሔርን ዐላማ ለማስፈጸም እንጂ እኛን ለመጕዳት ወይም ለማጥፋት አይደለም (ሐሥ11፥19፤ሮሜ 5፥3፤2ቆሮ1፥4፤ 4፥17 ይመ)።

3፥5 ***ፈታኙ፤*** በአዲስ ኪዳን ውስጥ በብዙ ቦታ ላይ ሰይጣን በዚህ ስም ተጠርቶአል። እርሱም የርኩሳን መናፍስት ሁሉ የበላይ ነው (ዮሐ16፥11፤ኤፌ2፥2 ይመ)፤ በድርጊቱም ቁሳዊውንና (2ቆሮ12፥7 ይመ) መንፈሳዊውን ነገር ይጎዳል (ማቴ13፥39፤ ማር4፥15፤2ቆሮ4፥4 ይመ)፤ እርሱ ኢየሱስን ፈትኖአል (ማቴ 4፥1-11 ይመ)፤ የኢየሱስንም አገልጋዮች በመፈተን ላይ ነው (ሉቃ22፥31፤1ቆሮ7፥5 ይመ)፤ የወንጌልን ሥርጭት ያደናቅፋል (2፥18)። ነገር ግን የተሸነፈ ስለ ሆነ (ቈላ2፥15 ይመ)፣ ክርስቲያኖች ዕድል ፈንታ ሊሰጡት አይገባቸውም (ኤፌ6፥16)። በመጨረሻም ለዘላለም መጣሉ የተረጋገጠ ነው (ራእ 20፥10 ይመ)።

3፥6 ***መልካም ዜና አሰምቶናል፤*** በግሪኩ "ወንጌል"የሚለው ቃል ከሚሰጠው ትርጕም የተለየ ሐሳብ ያለው ብቸኛ የግሪኩ ቋንቋ ሐረግ ነው። ጳውሎስ ለደስታው ምክንያት የሆኑትን ሦስት ነገሮች ጠቅሶአል፤ (1) "እምነታችሁ" ወደ እግዚአብሔር የሚወስድ ትክክለኛ ዝንባሌ፤ (2) "ፍቅራችሁ" ሰው ለሰው ሊኖረው ስለሚገባ ትክክለኛ ዝንባሌ፣ (3) "እኛን ለማየት እንደምትናፍቁ" ለጳውሎስ የነበራቸውን ትክክለኛ ዝንባሌ ያሳያል።

3፥9 ***ለእግዚአብሔር... ምስጋና፤*** ከዚህ በፊት ያለው ታሪክ የጳውሎስ የወንጌል አገልግሎት ስኬታማ እንደ ነበር ያሳያል። ሥራውን በተገቢው ሁኔታ በመሥራቱ ራሱን ሊያሞካሽ በተገባው ነበር፤ ነገር ግን እግዚአብሔር ከሠራው ሥራ የተነሣ ደስ በመሰኘት እግዚአብሔርን ያመሰግናል።

3፥10 ***በእምነታችሁ፤*** ጳውሎስ ስለ እምነታቸው በዚህ ምዕራፍ ለአምስተኛ ጊዜ መናገሩ ነው (ቁ.2፡5-7 ይመ)። ***የጐደለውን፤*** በዕለታዊ ሕይወታቸው የግብረ ገብነት (4፥1-12) እና የሥነ ሥርዐት (5፥12-24) ጕድለት እንዳለ ያመለክታሉ። ሌላው ደግሞ ከክርስቲያናዊ አስተምህሮ ጋር የተያያዘ ሲሆን በክርስቶስ ዳግም ምጽአት አንጻር የነበራቸውን ግራ መጋባት ያሳያል። ***ሌሊትና ቀን፤*** በሁለቱ ክፍለ ጊዜያት ብቻ ተወስኖ መጸለይን ሳይሆን ያለማቋረጥ መጸለይን ያሳያል (1፥2-3 ይመ)። ***እጅግ ተግተን፤*** ከልብ የሚመነጨውን የጳውሎስን ናፍቆትና ጕጕት ጠንከር ባለና ባልተለመደ የግሪክ አባባል የሚገልጽ ነው (ቃሉ በአዲስ ኪዳን በ5፥13 እንዲሁም በኤፌ 3፥20 ላይ ብቻ ይገኛል)።

*3፥11፤* ጳውሎስ ብዙ ጊዜ በመልእክቱ መካከል ጣልቃ እያስገባ ጸሎትን ያቀርባል (ኤፌ1፥15-23፤3፥14-21፤ፊል1፥9-11፤ ቈላ1፥9-12)። በአብና በወልድ መካከል ያለው ግንኙነት በተመለከተ የ1፥1 ማብ ይመ።

3፥12 ***ጌታ፤*** በጳውሎስ ጽሑፎች ውስጥ ይህ ቃል አብዛኛውን ጊዜ አብን ሳይሆን ኢየሱስን የሚያሳይ ነው።

3፥13 ***ቅዱሳኑ፤*** በብዙ የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ቅዱሳን የሚለው ቃል ክርስቲያኖችን ያመለክታል። እዚህ ቦታ የሚያመላክተው ግን ከክርስቶስ ጋር ተመልሰው የሚመጡትንና ወደ እርሱ የተወሰዱ ቅዱሳንን ወይም መላእክትን ወይም ደግሞ ሁለቱንም ሊሆን ይችላል (ማር8፥38)። ***ቅዱሳን፤*** መሠረታዊ ሐሳቡ "ለእግዚአብሔር የተለዩ" ማለት ነው፤ በዚህ ስፍራ ግን የቅድስናን የመጨረሻ ደረጃ ያሳያል (የ1ቆሮ 1፥2 ማብ ይመ)። ***ያጽና፤*** የቁ.2 ማብ ይመ።

4፥1 ***በቀረውስ፤*** ከዚህ የሚቀጥል ብዙ ነገር ቢኖርም የመልእክቱ

አስተምረናችኋል፤ በእርግጥም እንደዚያው እየኖራችሁ ነው። ስለ ሆነም በጌታ በኢየሱስ የምንለምናችሁና የምንመክራችሁ ከዚህ በበለጠ ሁኔታ በዚሁ እንድትገፉበት ነው። [2]በጌታ በኢየሱስ ሥልጣን ምን ዐይነት ትእዛዝ እንደ ሰጠናችሁ ታውቃላችሁ።

[3]የእግዚአብሔር ፈቃድ ከዝሙት ርቃችሁ እንድትቀደሱ ነው፤ [4]ደግሞም እያንዳንዱ የገዛ ሰውነቱን በቅድስናና በክብር መያዝ[w] እንዳለበት እንዲያውቅ ነው፤ [5]ይህም እግዚአብሔርን እንደማያውቁ አሕዛብ በፍትወት ሥጋ ምኞት አይሁን። [6]በዚህም ነገር ማንም ተላልፎ ወንድሙን አያታል፤ ምክንያቱም ከዚህ በፊት እንደነገርናችሁና እንዳስጠነቀቅናችሁ ጌታ እንደ እነዚህ ያለውን ኀጢአት ሁሉ የሚፈጽሙትን ይበቀላል፤ [7]እግዚአብሔር በቅድስና እንድንመላለስ እንጂ ለርኵሰት አልጠራንምና። [8]እንግዲህ ይህን ምክር ንቆ የማይቀበል፣ የናቀው ቅዱስ መንፈሱን የሰጣችሁን እግዚአብሔርን እንጂ ሰውን አይደለም።

[9]ስለ ወንድማማች መዋደድ ማንም እንዲጽፍላችሁ አያስፈልግም፤ ምክንያቱም እርስ በርሳችሁ እንድትዋደዱ እናንተ ራሳችሁ ከእግዚአብሔር ተምራችኋልና። [10]በመላዪቱ መቄዶንያ የሚገኙትን ወንድሞች ሁሉ እንደምትወዷቸው የታወቀ ነው፤ ነገር ግን ወንድሞች ሆይ፤ ከዚህ በበለጠ እንድትገፉበት እንመክራችኋለን።

[11]ከዚህ በፊት እንዳዘዝናችሁ በገዛ እጃችሁ ሥሩ፤ በጸጥታ ኑሩ፤ በራሳችሁ ጒዳይ ላይ ብቻ አተኩሩ። [12]ይኸውም በዕለት ተለት ኑሮአችሁ በውጭ ባሉት ዘንድ እንዲያስከብራችሁና በማንም ሰው ላይ ሸክም እንዳትሆኑ ነው።

1ተሰ2፥19፤5፥23፤
4፥3 1ቆሮ6፥18፤ ኤፌ5፥17
4፥4 1ቆሮ7፥2፡9
4፥5 ሮሜ1፥26፤ ገላ4፥8፤ኤፌ4፥17
4፥6 ዘሌ25፥17፤ ዘዳ32፥35፤መዝ94፥1፤ሮሜ2፥5-11፤ 12፥19፤1ቆሮ6፥8፤ ዕብ10፥30፡31፤13፥4
4፥7 ዘሌ11፥44፤ 1ጴጥ1፥15
4፥8 ሕዝ36፥27፤ ሮሜ5፥5፤2ቆሮ1፥22፤ ገላ4፥6፤1ዮሐ3፥24
4፥9 ዮሐ6፥45፤ 13፥34፤ሮሜ12፥10፤ 1ተሰ5፥1
4፥10 ሐሥ16፥9፤ 1ተሰ3፥12
4፥11 ኤፌ4፥28፤ 2ተሰ3፥10-12
4፥12 ማር4፥11
4፥13 ማቴ9፥24፤ ሮሜ11፥25፤ ኤፌ2፥12
4፥14 ሮሜ14፥9፤ 1ቆሮ15፥3፡4፤18፤2ቆሮ5፥15
4፥15 1ቆሮ1፥7፤ 15፥52

## ጌታ ዳግም ምጽአት

[13]ወንድሞች ሆይ፤ አንቀላፍተው ስላሉ ሰዎች ሳታውቁ እንድትቀሩ አንፈልግም፤ ደግሞም ተስፋ እንደ ሌላቸው እንደ ሌሎች ሰዎች እንድታዝኑ አንሻም። [14]ኢየሱስ እንደ ሞተና እንደ ተነሣ ካመንን በኢየሱስ ሆነው ያንቀላፉትን እግዚአብሔር ከእርሱ ጋር እንደዚሁ ያመጣቸዋል። [15]በጌታ ቃል የምንላችሁ ይህን ነው፤ እኛ በሕይወት ያለንና ጌታ እስኪመጣ ድረስ የምንቀር ያንቀላፉትን አንቀድምም፤

*[w]4 ወይም ከገዛ ሚስቱ ጋር መኖርን መማር ወይም ሚስት ለማግኘት መማር*

ዋና ክፍል ተጠናቅቆአል (ፊል3፥1 እና ማብ ይመ)። *መኖር፤* የቃሉ ቀጥተኛ ትርጒም፣ "መመላለስ" ማለት ነው፤ ጳውሎስ ብዙውን ጊዜ ይህን ተለዋጭ ዘይቤ የክርስትናን አካሄድ ለመግለጽ ይጠቀምበታል (ሮሜ6፥4፤2ቆሮ5፥7፤ኤፌ4፥1፤5፥17፤ቈላ1፥10 "ትኖሩ ዘንድ" 2፥6፤ 4፥5 "ተመላለሱ")። ይህ የማያቋርጥ እድገትን ያመለክታል። *የምንለምናችሁና የምንመክራችሁ፤* ጳውሎስ በትሕትና በጌታ ኢየሱስ በተሰጠው ሥልጣን መናገሩ ነው፤ ምክንያቱም፣ "የክርስቶስ ልብ" አለው (1ቆሮ 2፥16)።

4፥2 *ትእዛዝ፤* በሥልጣን የሚተላለፍን ትእዛዝ ይጠቁማል፤ ቃሉም ወታደራዊ አመራርን ያዘለ ነው (ሐሥ5፥28፤16፥24 ይመ)።

4፥3 *እንድትቀደሱ፤* የ3፥13 ማብ ይመ። *ከዝሙት፤* በመጀመሪያው ምእተ ዓመት የሥነ ምግባር ብልሹነት ተስፋፍቶ ነበር፤ ራስን በንጽሕና መጠበቅም አስፈላጊ እንዳልሆነ ተደርጎ ይቈጠር ነበር፤ ይሁን እንጂ ጳውሎስ የእግዚአብሔርን ግልጽ የምግባር መለኪያዎች ከዘመኑ ሁኔታ ጋር እንዲቀየጡ አልፈቀደም። ክርስቲያኖችም ሊፈተኑ ስለሚችሉ ማስጠንቀቅ አስፈላጊ ነበር (1ቆሮ 5፥1 ይመ)።

4፥5 *እንደማያውቁ አሕዛብ ፤* ክርስቲያኖች ከማያምኑ ሰዎች የተለዩ ሊሆኑ ይገባቸዋል።

4፥6 *ወንድሙን አያታል፤* የዝሙት ኀጢአት ድርጊቱን የሚፈጽሙትን ብቻ ሳይሆን ሌሎችንም ይጎዳል። ለምሳሌ የአመንዝራ ሰው የትዳር አጋር ሁልጊዜ ይበደላል፤ በቅድመ ጋብቻ የሚፈጸም የግብረ ሥጋ ግንኙነት እስከ ጋብቻው ቀን ድረስ ሊጠበቅ የሚገባውን ንጽሕና በማጒደፍ ወደ ፊት የትዳር ጓደኛ የሚሆነውን ሰው ይበድላል። *ጌታ...ይበቀላል፤* በንጽሕና ለመኖር የሚያበረታታ ነው።

*4፥7፤* የእግዚአብሔር የቅድስና ጥሪ በንጽሕና ለመኖር ሌላው ምክንያት ነው።

4፥8 *የማይቀበል......እግዚአብሔርን እንጂ ሰውን አይደለም፤* ሐዋርያው ስለ ቅድስናና ንጽሕና የሰጠውን ትእዛዝ የሚቃወም ወይም የሚያንቋሽሽ እግዚአብሔርን ይቃወማል። *ቅዱስ መንፈሱን የሰጣችሁን እግዚአብሔርን፤* በንጽሕና ለመኖር ሌላው ምክንያት ደግሞ የዝሙትን ኀጢአት መፈጸም አማኞች በቅድስና እንዲኖሩ መንፈስ ቅዱስን በሰጠው በእግዚአብሔር ላይ የሚሠራ ዐመፅ በመሆኑ ነው።

4፥9 *ከእግዚአብሔር ተምራችኋልና፤* ከኢሳ54፥13፤ ዮሐ 6፥45፤ ከ1ቆሮ2፥13 ጋር ያነጻጽሩ። *ስለ ወንድማማች መዋደድ፤* በግሪኩ ፊላደልፊያ ማለት ሲሆን ከአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውጭ ቃሉ የአንድ አባት ልጆች በሆኑ ሰዎች መካከል ያለውን የፍቅር አንድነት ያሳያል። በአዲስ ኪዳን ግን አንድ ሰማያዊ አባት ባላቸውና በክርስቶስ በሚያምኑ ሰዎች መካከል ያለውን ፍቅር ያመለክታል።

*4፥11፤* አንዳንድ የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች ምናልባት ሥራ ከመፍታታቸው የተነሣ በሌሎች ሰዎች ጒዳይ ጣልቃ የመግባት ልማድ ሳይኖራቸው አይቀርም። *በገዛ እጃችሁ ሥሩ፤* በግሪኮች ዘንድ በአጠቃላይ በእጅ የሚሠራ የጒልበት ሥራ ሁሉ የሚያዋርድና ባሪያዎች ብቻ እንዲሠሩት የተገባ እንደ ሆነ ይታሰባል። ክርስቲያኖች በገዛ እጃቸው እየሠሩ የራሳቸውን ኑሮ ሊመሩ ሲገባቸው አንዳንድ የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች ግን የክርስቶስ ዳግም ምጽአት በቅርብ ይሆናል የሚል እምነት ስለ ነበራቸው (2ተሰ3፥11) ሥራ መሥራት ትተው በሌሎች ላይ ጥገኛ በመሆን ይኖሩ ነበር።

4፥12 *በማንም ሰው ላይ ሸክም እንዳትሆኑ፤* ወይም "ማንም ሳያስፈልጋችሁ" ማለት ነው። ሁለቱም ትርጒሞች እውነተኛና ጠቃሚ ናቸው። በሥራ ፈትነታቸው ምክንያት በችግር ላይ የሚወድቁ ክርስቲያኖች ለእግዚአብሔር የሚታዘዙ አይደሉም።

4፥13 *አንቀላፍተው ስላሉ ሰዎች፤* የሞት የበላይነትና አስፈሪነት በትንሣኤ ኀይል ስለ ተሻረ፣ "እንቅልፍ" ለክርስቲያኖች ሞትን የሚያመለክት ተለዋጭ ዘይቤ ነው። አንዳንድ የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች፣ አማኞች ሁሉ ክርስቶስ እስኪመጣ ድረስ አይሞቱም በማለት የጳውሎስን ትምህርት በተሳሳተ መንገድ ተረድተውት ነበር። ከመካከላቸው አንዳንዶች በሞቱ ጊዜም፣ "እነዚህ የሞቱ ሰዎች በታላቁ ቀን ድርሻ ይኖራቸው ይሆን?" የሚል ጠያቂ ያነሡ ነበር (የቍ15 ማብ ይመ)። *ተስፋ እንደ ሌላቸው፤* በመቃብር ድንጋይ ላይ የተጻፉና ቀድሞ የነበሩ ጽሑፎች እንደሚያሳዩት፣ በመጀመሪያ ምእተ ዓመት የነበሩ አረማውያን ሞት እጅግ አስፈሪና የሁሉ ነገር መጨረሻ እንደ ሆነ ያስቡ ነበር። የክርስቲያኖች አመለካከት ግን ከዚህ ፍጹም የተለየ ነው (1ቆሮ15፥55-57፤ ፊል1፥21-23 ይመ)።

4፥14 *ሞተ፤* በዚህ ክፍል ጳውሎስ፣ ክርስቶስ "አንቀላፋ" አላለም፤ ምክንያቱም በእርሱ የሚያምኑ ሁሉ ከሞት ፍርሀት ነጻ ይሆኑ ዘንድ ክርስቶስ መሞቱን በጒልህ ማሳየት ተገቢ በመሆኑ ሊሆን ይችላል። *ተነሣ፤* ትንሣኤን በሚመለከት 1ቆሮንቶስ15 በተለይም ቍጥር 14፡17-22 ይመ። *በኢየሱስ... ያንቀላፉትን፤* በኢየሱስ አምነው የሞቱትን አማኞች ያመለክታል።

4፥15 *በጌታ ቃል፤* በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው የክርስትና ትምህርት በወንጌላት ውስጥ የተጻፈ አይደለም፤ ነገር ግን ለጳውሎስ በቀጥታ በራእይ የተገለጠለት ወይም በቃል ሲተላለፍ የመጣ ክርስቶስ ለክርስቲያኖች የተናገረው ሊሆን ይችላል። *እኛ በሕይወት ያለን፤* ክርስቶስ ዳግም ሲመጣ በሕይወት የሚገኙትን ክርስቲያኖች ያመለክታል፤ "እኛ" የሚለው ቃል እስከ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት ድረስ ጳውሎስ በሕይወት እንደሚኖር አስቦ የተናገረው ላይሆን ይችላል። ብዙ ጊዜ መልእክቱን ከጻፈላቸው ሰዎች ጋር ራሱን ያመሳስላል። በሌላ ስፍራ እግዚአብሔር "እኛን" በዚያን ጊዜ ያስነሣናል በማለት ተናግሮአል (1ቆሮ6፥14፤2ቆሮ4፥14)። *አንቀድምም፤* የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች ከመካከላቸው የሞቱት ሰዎች ጌታ ተመልሶ በሚመጣበት ታላቅ ቀን ስፍራቸውን ያጣሉ ብለው ስለ ተጨነቁ ይህ እንደማይሆን ጳውሎስ ያረጋግጥላቸዋል።

[16]ጌታ ራሱ በታላቅ ትእዛዝ፣ በመላእክት አለቃ ድምፅና በእግዚአብሔር የመለከት ድምፅ ከሰማይ ይወርዳልና፡፡ በክርስቶስ የሞቱ ትም አስቀድመው ይነሣሉ፡፡ [17]ከዚያም በኋላ እኛ የቀረነው፣ በሕይወትም የምንኖረው ጌታን በአየር ላይ ለመቀበል ከእነርሱ ጋር በደመና እንነጠቃለን፤ በዚህም መሠረት ለዘላለም ከጌታ ጋር እንሆናለን፡፡ [18]ስለዚህ በዚህ ቃል እርስ በርሳችሁ ተጽናኑ፡፡

**5** ወንድሞች ሆይ፤ ስለ ዘመናትና ስለ ወራት ልንጽፍላችሁ አያስፈልግም፡፡ [2]ምክንያቱም ሌባ በሌሊት እንደሚመጣ የጌታም ቀን እንዲሁ እንደሚመጣ እናንተ ራሳችሁ በሚገባ ታውቃላችሁ፡፡ [3]ሰዎች፣ “ሰላምና ደኅንነት ነው’ ሲሉ፣ ምጥ እርጉዝ ሴትን እንደሚይዛት እንዲሁ ጥፋት በድንገት ይመጣባቸዋል፤ ከቶም አያመልጡም፡፡

[4]እናንተ ግን፣ ወንድሞች ሆይ፤ ይህ ቀን እንደ ሌባ ያስደንግጣችሁ ዘንድ በጨለማ ውስጥ አይደላችሁም፤ [5]ሁላችሁም የብርሃን ልጆች፣ የቀንም ልጆች ናችሁና፡፡ እኛ ከሌሊት ወይም ከጨለማ ወገን አይደለንም፤ [6]እንግዲህ እንንቃ፤ ራሳችንንም እንግዛ እንጂ እንደሚያንቀላፉት እንደ ሌሎቹ አንሁን፡፡ [7]የሚያንቀላፉ በሌሊት ያንቀላፋሉ፤ የሚሰክሩም በሌሊት ይሰክራሉና፡፡ [8]እኛ ግን የቀን ሰዎች ስለ ሆንን፣ እምነትንና ፍቅርን እንደ ጥሩር ለብሰን፣ የመዳንን ተስፋ እንደ ራስ ቍር ደፍተን ራሳችንን በመግዛት እንኑር፤ [9]እግዚአብሔር ድነትን በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት እንድናገኝ ነው እንጂ ለቍጣ ወስኖ አላስቀመጠንምና፡፡ [10]ብንነቃም ሆነ ብናንቀላፋ ከእርሱ ጋር በሕይወት እንድ ንኖር እርሱ ስለ እኛ ሞተ፡፡ [11]ስለዚህ በእርግጥ አሁን እንደምታደርጉት ሁሉ እርስ በርሳችሁ ተጽናኑ፤ አንዱም ሌላውን ያንጽ፡፡

## የመጨረሻ ምክር

[12]እንግዲህ ወንድሞች ሆይ፤ በእናንተ መካከል በትጋት የሚሠሩትን፣ በጌታም የበላ ዮቻችሁና መካሪዎቻችሁ የሆኑትን እንድታ ከብሯቸው እንለምናችኋለን፤

4፥16 ማቴ16፥27፤ 24፥31፤1ቆሮ15፥23፤ 2ተሰ2፥1፤ይሁ9፤ ራእ14፥13
4፥17 ዮሐ12፥26፤ ሐሥ1፥9፤8፥39፤ 1ቆሮ15፥52፤ ራእ1፥7፤11፥12
4፥18 1ተሰ5፥11
5፥1 ሐሥ1፥7፤ 1ተሰ4፥9
5፥2 ሉቃ12፥39፤ 1ቆሮ1፥8
5፥3 ኢዮ15፥21፤ መዝ35፥8፤55፥15፤ ኢሳ29፥5፤47፥9፡11፤ ኤር4፥10፤6፥14፤ ሕዝ13፥10፤2ተሰ1፥9
5፥4 ቍ2፤ ሐሥ26፥18፤ 1ዮሐ2፥8
5፥5 ሉቃ16፥8
5፥6 ማቴ25፥13፤ ሐሥ24፥25፤ ሮሜ13፥11
5፥7 ሐሥ2፥15፤ ሮሜ13፥13፤ 2ጴጥ2፥13
5፥8 ቍ5፤ ኢሳ59፥17፤ ሮሜ24፤ኤፌ6፥14፡17
5፥9 1ተሰ1፥10፤ 2ተሰ2፥13፡14
5፥10ሮሜ14፥9፤2ቆሮ5፥15
5፥11ኤፌ4፥29፤ 1ተሰ4፥18
5፥12ሮሜ16፥6፡12፤ 1ቆሮ15፥10፤1ጢሞ5፥17፤ዕብ13፥17

4፥16 *ጌታ ራሱ፤* ሐሥ1፥11 ይመ፡፡ *በመላእክት አለቃ፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የተጠቀሰው ብቸኛው የመላከት አለቃ ሚካኤል ነው (ይሁዳ 9፤ ዳን10፥13)፤ በመጽሐፍ ቅዱስ ገብርኤል መልአክ እንደ ሆነ ተገልጾአል (ሉቃ1፥19፡26)፡፡ *አስቀድመው ይነሣሉ፤* በሚቀጥለው ቍጥር ላይ የተጠቀሱት አማኞች ከመነጠ ቃቸው በፊት ማለት ነው፡፡

4፥17 *በሕይወትም የምንኖረው፤* የቍ15 ማብ ይመ፡፡ *እንነጠቃለን፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ ስለ መነጠቅ በግልጽ የተጻፈበት ብቸኛ ቦታ ነው፡፡ አንዳንዶች ይህ በስውር እንደሚሆን ሲናገሩ ሌሎች ግን በግልጽ የሚፈጸም ነው ይላሉ፡፡ *ከጌታ ጋር፤* የአማኞች ታላቅ ተስፋ ከጌታ ጋር መሆን ነው (5፥10፤ ዮሐ14፥3፤ 2ቆሮ5፥8፤ ፊል1፥23፤ ቈላ 3፥4 ይመ)፡፡

4፥18 *እርስ በርሳችሁ ተጽናኑ፤* የቍጥር 13-18 ዋና ሐሳብ ሊመጣ ስላለው ክስተት ቅደም ተከተል ማመልከት ሳይሆን፣ በዚህ ክፍልና በቍ13 ላይ እንደ ተጠቀሰው ምእመናን እርስ በርሳቸው እንዲበረታቱ ማድረግ ነው፡፡ ሐዋርያው የተሰሎንቄ ክርስ ቲያኖች እንዲበረታቱ የሚጽፍላቸው ሊመጣ ላለው መከራ እንዲ ዘጋጁ ሳይሆን (5፥2-10) በንጥቀት ጊዜ ከጌታ ጋር እንደሚሆኑ ለመግለጽ ነው፡፡

5፥1 *ስለ ዘመንናትና ስለ ወራት፤* ሐሥ1፥6-7 ይመ፡፡ የጌታችን መምጫ ቀን መቼ እንደ ሆነ ለማመልከት የሞከሩ አንዳንድ ክርስቲያኖች አሉ፤ በተሰሎንቄ ክርስቲያኖች መካከል ግን እንዲህ ዐይ ነቱ ችግር ያለበት ሰው ያለ አይመስልም ፡፡

5፥2 *የጌታም ቀን፤* 1ቆሮ5፥5 ይመ፡፡ ይህ ቃል የተወሰደው ከአሞጽ 5፥18 ነው፡፡ በብሉይ ኪዳን እግዚአብሔር በፍርድ ወይም ደግሞ በበረከት በመምጣት ጣልቃ የሚገባበትን ጊዜ ያመለክታል፡፡ በአዲስ ኪዳንም የፍርድ ሐሳብ አለ (ሮሜ2፥5፤ 2ጴጥ 2፥9)፤ ይህም “ቀን” (ኤፌ4፥30)፣ ‘የእግዚአብሔር ቀን’ (2ጴጥ 3፥12) ወይም “የክርስቶስ ቀን” (1ቆሮ1፥8፤ፊል1፥6) እና “የመጨረሻ ቀን” (ዮሐ 6፥39)፣ “ታላቅ ቀን” (ይሁዳ 6) ወይም “ያ ቀን” በመባል ይታወቃል (2 ተሰ1፥10)፡፡ ይህ የሁሉ ነገር ፍጻሜ ነው፡፡ ቀደም ያሉ ምልክቶች ሊኖሩ ቢችሉም (2ተሰ 2፥3)፣ ዳግም ምጽአቱ ግን ሌባ በሌሊት እንደሚመጣ ሳይታሰብ የሚሆን ነው (ከማቴ 24፥43-44፤ ሉቃ12፥39-40፤ 2ጴጥ3፥10፤ ራእ 3፥3፤ 16፥15 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡

5፥3 *ሰላምና ደኅንነት፤* ይህን የሚሉት የማያምኑ ሰዎች ናቸው፡፡ ይህም፣ ዓለም ሰላምን እንደምትጠብቅና ተስፋ እንደምታደርግ ያመለክታል፡፡ ነገር ግን የጌታ ቀን ድንገት ሲመጣ የሰላሙና የደኅንነቱ ተስፋ ይጠፋል፡፡ *ምጥ፤* እዚህ ቦታ የተጠቀሰው በወሊድ ጊዜ ያለውን ድንገተኛውንና ሊቀር የማይችለውን ምጥ ነው፡፡ *ጥፋት፤* ብን ብሎ መጥፋትን ሳይሆን ከጌታ ፊት መወገድን የሚያሳይ ነው (2ተሰ 1፥9)፤ *በድንገት፤* ጳውሎስ የማያምኑ ሰዎች ያላቸውን መደነቅ በአጽንዖት ይገልጻል፡፡ ቃሉ ከሉቃስ 21፥34 ላይ በስተቀር በየትኛውም የአዲስ ኪዳን መጽሐፍ ውስጥ አይገኝም ፡፡

5፥4 *ሌባ፤* የቍ 2 ማብ ይመ፡፡ *በጨለማ፤* አማኞች በጨለማ ውስጥ የሚኖሩ አይደሉም፤ የጨለማም ወገንም አይደሉም (ቍ 5)፡፡ ዮሐ1፥5፤ሐሥ 26፥18 ይመ፡፡

*5፥5፤* እንደ ዕብራይስጥ ባሉ ሴማዊ ቋንቋዎች፣ የአንድ ነገር “ልጅ” መሆን ማለት፣ የአባቱን ባሕርይ መያዝ ማለት ነው፡፡ እንደዚሁም ክርስቲያኖች በብርሃን የሚመላለሱ ብቻ ሳይሆኑ ብርሃን እንደሆኑ ያመለክታል፡፡

5፥6 *እንንቃ፤* በቋሙ ነቅተን እንጠብቅ ማለት ነው፤ ይህም ጳውሎስ የክርስቶስን መምጣት በንቃት እንድንጠባበቅ በአጽን ዖት መናገሩን የሚያሳይ ነው (ከማቴ24፥42-43፤25፥13፤ ማር13፥34-37 ጋር ያነጻጽሩ)፡፡ *ራሳችንንም እንግዛ፤* በቍ 7 ላይ ከተገለጸው ባሕርይ ጋር የሚነጻጸር ነው፡፡ *እንደሚያንቀላፉት፤* የማያምኑ ሰዎች በመን ፈሳቸው ሙታን ናቸው፤ ይህ ዐይነቱ እንቅልፍ ግን “የብርሃን ልጆች” ባሕርይ አይደለም፡፡

5፥8 *የቀን፤* የክርስቲያኖችን ባሕርይ የሚያሳየውን ብርሃን ያመለክታል፤ ምናልባትም የክርስቶስን መምጣት ሊያሳይ ይችላል (ቍ2እና ማብ ይመ)፡፡ *ጥሩር...ቍር፤* ጳውሎስ በሮሜ 13፥12፤ 2ቆሮ 6፥7፤10፥4፤ ኤፌ6፥13-17 ላይ የጦር መሣሪያን በተለዋዋጭ ዘይቤነት ተጠቅሞአል፡፡ አጠቃቀሙም ለእያንዳንዱ የጦር መሣሪያ የተወሰነ የአገልግሎት ድርሻ በመስጠት ሳይሆን፣ በአጠቃላይ ሐሳቡ ለውጊያ የሚያስፈልገውን የጦር መሣሪያ በመጥቀስ ነው፡፡ ስለ እምነት፣ ተስፋና ፍቅር በአንድ ላይ መጣመር የ1፥3 ማብ ይመ፡፡

5፥9 *ድነትን፤* የመጨረሻውንና ፍጹሙን መዳናችንን ያሳያል፡፡ *ቍጣ፤* የ1፥10 ማብ ይመ፡፡ *ወስኖ፤* ዋነኛውና መሠረታዊው ነገር የእግዚአሔር ውሳኔ እንጂ የሰው ምርጫ አይደለም፡፡

5፥10 *ከእርሱ ጋር፤* የክርስቶስ መሆን ፍጹም ሊጠፋ ወደ ማይችል ኅብረት ውስጥ መግባት ማለት ነው፡፡ ሐዋርያው የድነታችንን ተስፋና ከእግዚአብሔር ቍጣ መዳናችንን፣ ከክርስቶስ የመሥዋዕትነት ሞት እንዲሁም ከእርሱ ጋር እንድንኖር ሊወስደን ከመምጣቱ ጋር በማዛመድ ያቀርባል፡፡ *ብንነቃም ሆነ ብናንቀላፋ፤* “ብንኖር ወይም ብንሞት” ወይም ደግሞ ትምህርቱ የሥነ ምግባር ጕዳይ ከሆነ፣ ብንነቃ ወይም ሥጋዊ ክርስቲያን ብንሆን (ቍ6) ማለት ነው፡፡

5፥11 *ያንጽ፤* ግሱ ቤት ከመመሥረት ጋር አብሮ የሚሄድ ቢሆ ንም እንኳ ጳውሎስ ክርስቲያን በመንፈሳዊው ነገር ስለሚኖረው አንድነት መታነጽ ለማሳየት ቃሉን ደጋግሞ ተጠቅሞአል ፡፡

5፥12 *በእናንተ መካከል በትጋት የሚሠሩትን፤* በዚህ ወቅት ስለ ቤተ ክርስቲያን አስተዳደርና አመራር ብዙ የሚ ታወቅ ነገር ባይኖርም፣ ይህ የቤተ ክርስቲያን ሽማግሌዎችን የሚያሳይ ሳይሆን አይቀርም፡፡

[13]ስለ ሥራቸውም በፍቅር እጅግ አክብሯቸው። እርስ በርሳችሁም በሰላም ኑሩ። [14]ወንድሞች ሆይ፤ ይህን እንመክራችኋለን፤ ሥራ ፈቶችን ገሥጿቸው፤ ፈሪዎችን አደፋፍሯቸው፤ ደካሞችን እርዷቸው፤ ሰውን ሁሉ ታገሡ። [15]ማንም በክፉ ፈንታ ክፉ እንዳይመልስ ተጠንቀቁ፤ ነገር ግን እርስ በርሳችሁም ሆነ ለሌሎች ሰዎች ሁልጊዜ መልካም የሆነውን ነገር ለማድረግ ተጣጣሩ።

[16]ሁልጊዜ ደስ ይበላችሁ፤ [17]ሳታቋርጡ ጸልዩ፤ [18]በማናቸውም ሁኔታ አመስግኑ፤ የእግዚአብሔር ፈቃድ በክርስቶስ ኢየሱስ ለእናንተ ይህ ነውና።

[19]የመንፈስን እሳት አታዳፍኑ፤ [20]ትንቢትን አትናቁ። [21]ሁሉን ነገር ፈትኑ መልካም የሆነውን ያዙ፤ [22]ከማናቸውም ዐይነት ክፉ ነገር ራቁ።

[23]የሰላም አምላክ ራሱ ሁለንተናችሁን ይቀድስ፤ መንፈሳችሁ፣ ነፍሳችሁና ሥጋችሁ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በሚመጣበት ጊዜ ያለነቀፋ ይጠበቅ። [24]የጠራችሁ የታመነ ነው፤ እርሱም ያደርገዋል።

[25]ወንድሞች ሆይ፤ ስለ እኛ ደግሞ[ሀ] ጸልዩ። [26]ወንድሞችን ሁሉ በተቀደሰ አሳሳም ሰላም በሏቸው። [27]ይህ መልእክት ለወንድሞች ሁሉ እንዲነበብ በጌታ ዐደራ እላችኋለሁ።

[28]የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ከእናንተ ጋር ይሁን።

5፥13 ማር9፥50
5፥14 ሮሜ14፥1፤ 1ቆሮ8፥7-12፤ 2ተሰ3፥6፡7፡11
5፥15 ሮሜ12፥17፤ ኤፌ4፥32፤1ጴጥ3፥9
5፥16 ፊል4፥4
5፥17 ሉቃ18፥1
5፥18 ኤፌ5፥20
5፥19 ኤፌ4፥30
5፥20 1ቆሮ14፥1-40
5፥21 ሮሜ12፥9፤ 1ቆሮ14፥29፤ 1ዮሐ4፥1
5፥23 ሮሜ15፥33፤ 1ተሰ2፥19፤3፥13፤ ዕብ4፥12
5፥24 ዘኍ23፥19፤ ሮሜ8፥28፤ 1ቆሮ1፥9፤ፊል1፥6
5፥25 6፥19፤ ቈላ4፥3፤2ተሰ3፥1፤ ዕብ13፥18
5፥26 ሮሜ16፥16
5፥27 2ተሰ3፥14፤1ጢሞ4፥13
5፥28 ሮሜ16፥20

[ሀ]25 አንዳንድ ትርጒሞች ደግሞ የሚለው ቃል የላቸውም

5፥13 *ስለ ሥራቸውም፤* በግል ከመቀራረብ የተነሣ ወይም ሥልጣን ስላላቸው ብቻ ሳይሆን ስለ ሥራቸው ስትሉ ማለት ነው። *በሰላም ኑሩ፤* ሐሳቡ በአጠቃላይ በክርስቲያኖች መካከል ስላለው ኅብረት የሚናገር ቢሆንም፣ እዚህ ላይ ግን በመሪዎችና በእነርሱ ሥር በሚተዳደሩ መካከል ሊኖር ስለሚገባው ትክክለኛ ኅብረት ያመለክታል።

5፥14 *ሥራ ፈቶች፤* አንዳንድ የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች የክርስቶስ ዳግም ምጽአት በቅርቡ እንደሚሆን እርግጠኞች ሆነው ለዝግጅት ሥራቸውን እርግፍ አድርገው የተዉ ይመስላል፤ ስለ ለዚህ እንዲሠሩ ይነግራቸዋል። *ፈሪዎችን...ደካሞችን፤* እነዚህ በብርቱዎች ሊደገፉና ሊረዱ እንጂ ሊጣሉ አይገባም (ከሮሜ14፥1-15፤1ቆሮ 8፥13 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥15 *እንዳይመልስ፤* ብቀላ ለክርስቲያኖች አማራጭ ሆኖ ሊቀርብ አይችልም (ከሮሜ12፥17፤1ጴጥ3፥9 ጋር ያነጻጽሩ። ክርስቲያኖች ይቅርታ እንዲያደርጉ ተጠርተዋል (ማቴ5፥38-42፤18፥21-35)።

*5፥16፤* ሰዎች በአንዳንድ ሁኔታዎች ደስተኞች ይሆናሉ፤ የክርስቲያኖች ደስታ ግን በሁኔታዎች ላይ የተመሠረተ አይደለም። ደስታቸው የሚመነጨው ክርስቶስ ከሠራው ሥራ ነው፤ ይህም ደግሞም ዘላቂ ነው።

*5፥17፤* ያለ ማቋረጥ ስለሚደረግ ጸሎት 1፥3፤2፥13፤ ሮሜ 1፥9-10፤ ኤፌ6፥18፤ ቈላ1፥3፤ 2ጢሞ 1፥3 ይመ።

*5፥18፤* በቍ16 እንደተገለጸው፣ ክርስቲያኖች በሁኔታ ላይ ከተመሠረቱ ከተፈጥሮአዊ ሰዎች የተለዩ ናቸው። ምክንያቱም በየትኛውም ሁኔታ ውስጥ ቢሆኑ እንኳ እግዚአብሔር ካደረገላቸው ነገር የተነሣ የሚያመሰግኑ ናቸው (ከኤፌ5፥20 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥19 *የመንፈስን እሳት፤* ይህን አባባል እውነት የሚያደርገው በመንፈስ ቅዱስ መገኘት ሙቀትና ብርሃን መኖሩ ነው። ጳውሎስ የተቃወማቸው ባሕርያት ሥራ ፈትነትን፣ ዝሙትንና ሌሎችንም ኀጢአቶች ነው። በሌላ በኩል ደግሞ በጉባኤ ውስጥ የመንፈስ ቅዱስን ስጦታ የሚያዳክም ሥጋዊ የሆነ አምልኮ እንዳይደረግ ያስጠነቅቃል (ቍ20 ይመ)።

5፥20 *ትንቢት፤* ስለ ትንቢት ስጦታ ሮሜ12፥6፤ 1ቆሮ 12፥10፡28፤ 13፥2፡ 14፤ ኤፌ4፥11 ይመ። ስለ ትንቢት መናገር አገልግሎት ደግሞ 1ቆሮ14፥3 ይመ።

5፥21 *ሁሉን ነገር ፈትኑ፤* ትንቢት መናገር ተገቢ ቢሆንም (ቍ 20)፣ በጌታ ስም እናገራለሁ የሚል ሁሉ ያለ ምንም ጥያቄ ተቀባይነት ያገኛል ማለት አይደለም። ጳውሎስ መፈተኛዎቹን በግልጽ ባያስቀምጥም እንኳ እያንዳንዱ ትምህርት መፈተን እንዳለበት ጽፎአል።

5፥23 *የሰላም አምላክ፤* ከቍ12-15 አንጻር እግዚአብሔርን የሚያመለክት ነው፤ ጳውሎስ በመልእክቶቹ መጨረሻ ላይ ብዙ ጊዜ በእንደዚህ ዐይነት መንገድ ስለ እግዚአብሔር ይጽፋል (ሮሜ 15፥33፤ 16፥20፤ 1ቆሮ14፥33፤ 2ቆሮ13፥11፤ ፊል4፥9 ይመ፤ ከ2ተሰ 3፥16 ጋር ያነጻጽሩ)። *መንፈሳችሁ፣ ነፍሳችሁና ሥጋችሁ፤* ጳውሎስ የሰውን ሁለንተና ሳይነጣጥል በአጽንዖት ያቀርባል።

*5፥24፤* ጳውሎስ የሚተማመነው የጀመረውን ከፍጻሜ በሚያደርሰው በእግዚአብሔር ላይ ነው (ከዘፍ18፥25 ጋር ያነጻጽሩ፤ ዘኍ23፥19፤ፊል1፥6 ይመ)።

5፥26 *ሁሉ፤* ጳውሎስ ሰላምታውን የላከው የገሠጻቸውን ሰዎች ጨምሮ ለሁሉም ነው። *በተቀደሰ አሳሳም፤* በዚህ ዘመን እጅ በመጨባበጥና በመሳሳም ሰላምታ እንደምንለዋወጥ ሁሉ፣ በዚያን ዘመን በመሳሳም ሰላምታ ይለዋወጡ ነበር (ከሮሜ 16፥16፤ ከ1ቆሮ 16፥20፤ 2ቆሮ13፥12 ጋር ያነጻጽሩ፤ በ1ጴጥ 5፥14ላይ "የፍቅር አሳሳም" የሚለውን ይመ)።

5፥27 *ዐደራ እላችኋለሁ፤* ጠንከር ያለ አባባል ሲሆን "አምላችኋለሁ" ማለት ነው። ጳውሎስ፣ የተሰሎንቄ ቤተ ክርስቲያን ምእመናን በሙሉ የእርሱን መልእክት እንዲያነቡ ወይም እንዲሰሙ እንዲሁም እንደሚያስብላቸው እንዲያውቁና የሚሰጠውንም ምክር እንዲቀበሉ ይፈልጋል።

*5፥28፤* ጳውሎስ ሁልጊዜ መልእክቶቹን የሚደመድመው ለአንባቢዎቹ የጸጋ ቡራኬ በመስጠት ሲሆን አንዳንድ ጊዜም ሌሎች በረከቶችን ይጨምራል (2ቆሮ 13፥14)።

# የሐዋርያው ጳውሎስ መልእክት
# ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች - ሁለተኛ

## መግቢያ

የ1ኛ ተሰሎንቄን መግቢያ ይመ

**ጸሐፊው፣ መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ**

የጥንት ክርስቲያን ጸሐፊዎች ከሚሰጡት ሰፊ ድጋፍ በስተቀር በአንዳንዶች ዘንድ የጳውሎስ ጸሐፊነት ከ1ኛ ተሰሎንቄ ይልቅ በ2ኛ ተሰሎንቄ ላይ አጠያያቂነቱ የጐላ ነው:: ተቃዋሚዎቹ መሠረት የሚያደርጉት የቤተ ክርስቲያን አባቶች በሚሰጡት ምስክርነት ብቃት ላይ ያተኮረ ሳይሆን፣ በውስጥ መረጃዎች ላይ ነው፤ በቃላት (በሌላ ስፍራ የማይገኙ ዐሥር ቃላት እዚህ አሉ)፣ በአጻጻፉ ስልትና (ከሚጠበቀው በላይ መደበኛ ስልት ይጠቀማል) ስለ ዓለም መጨረሻ በሚያቀርበው አሳብ ላይ (ስለ ዐመፅ ሰው የተሰጠው ትምህርት በመጽሐፍ ቅዱስ በሌላ ስፍራ አልተሰጠም):: ይህ መልእክት ከመጀመሪያው እንደሚለይ የሚናገሩ አሉ፤ ይሁን እንጂ እነዚህ ምክንያቶች በወቅቱ የነበሩትን ምሁራን ሊያሳምኑ አልቻሉም:: አሁንም አብዛኞቹ ምሁራን የ2ኛ ተሰሎንቄ ጸሐፊ ጳውሎስ መሆኑን ያምናሉ፤ ሁለቱ መልእክታት ተመሳሳይነት ስላላቸው የተጻፉበትም ጊዜ ተቀራራቢ ሳይሆን አይቀርም፤ ምናልባትም ሁለተኛው መልእክት የተጻፈው የመጀመሪያው መልእክት ከተጻፈ ከስድስት ወር በኋላ ሊሆን ይችላል:: በወቅቱ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የነበረው ሁኔታ በሁለቱም መልእክታት ተመሳሳይ ነው፤ ጳውሎስ ይህን መልእክት የጻፈው (1፥1፤3፥17) በ51/44 ወይም በ52/45 በቆሮንቶስ ሳለ ሳይሆን አይቀርም፤ በዚህ ጊዜ ሲላስና ጢሞቴዎስ የመጀመሪያውን የተሰሎንቄ መልእክት አድርሰው ተመልሰዋል ::

**ዐላማው**

በተሰሎንቄ ቤተ ክርስቲያን የነበረው ሁኔታ ብዙም ያልተለወጠ ስለ ነበር፣ ጳውሎስ ይህን መልእክት የጻፈበት ዐላማና የመጀመሪያውን መልእክት የጻፈበት ዐላማ በጣም ተመሳሳይ ነው::
ጳውሎስ ይህን መልእክት የጻፈው:-

(1) በስደት ያሉትን አማኞች ለማፅናናት (1፥4-10)፣
(2) የተሰሎንቄ ሰዎች ታማኞች እንዲሆኑ፣ ለኑሮአቸውም ተግተው እንዲሠሩ ለመምከር (2፥13-3፥15)፣
(3) ስለ ጌታ ዳግም ምጽአት የነበራቸውን የተዛባ ግንዛቤ ለማስተካከል ነው (2፥1-12)::

**መሪ ሐሳቡ**

እንደ 1ኛ ተሰሎንቄ ይህም መልእክት በስፋት ስለ ነገረ ፍፃሜ ይተነትናል (ከ1ኛ ተሰሎንቄ መግቢያ ላይ፣ "መሪ ሐሳብ" የሚለውን ይመ) ፤ እንዲያውም በ2ኛ ተሰሎንቄ ውስጥ ካሉት 47 ጥቅሶች 18ቱ ማለትም 38% የሚሆኑት በዚህ ርእስ ላይ የሚናገሩ ናቸው::

**አስተዋፅኦ**

1 **መግቢያ (ም 1)**

ሀ ሰላምታ (1፥1-2)
ለ ስለ እምነታቸው፣ ስለ ፍቅራቸውና ስለ ጽናታቸው የቀረበ ምስጋና (1፥3-10)
ሐ በመንፈሳዊ ሕይወታቸው እንዲያድጉ የቀረበ ጸሎት (1፥11-12)

2 **ትምህርት (ም 2)**

ሀ ስለ ጌታ ቀን የተነገረ ትንቢት (2፥1-12)
ለ ስለ መመረጣቸውና ስለ መጠራታቸው ምስጋና (2፥13-15)
ሐ ስለ አገልግሎታቸውና ስለ ምስክርነታቸው ጸሎት (2፥16-17)

3 **የተለያዩ ትእዛዛት (ም 3)**

ሀ ለጸሎት የተደረገ ጥሪ (3፥1-3)
ለ ያለ ሥርዐት ለሚሄዱና ለሰነፎች የተሰጠ ማስጠንቀቂያ (3፥4-15)
ሐ ማጠቃለያ ሰላምታና ቡራኬ (3፥16-18)

**1** ጳውሎስ፣ ሲላስና[a] ጢሞቴዎስ፤

በእግዚአብሔር በአባታችን በጌታም በኢየሱስ ክርስቶስ ለሆኑት፣ ለተሰሎንቄ ሰዎች ቤተ ክርስቲያን፤

[2]ከእግዚአብሔር አብ፣ ከጌታ ከኢየሱስ ክርስቶስም ጸጋና ሰላም ለእናንተ ይሁን።

## የምስጋናና የልመና ጸሎት

[3]ወንድሞች ሆይ፤ እምነታችሁ በየጊዜው እያደገ በመሄዱና የእርስ በርስ ፍቅራችሁም እየጨመረ በመምጣቱ ስለ እናንተ እግዚአብሔርን ሁልጊዜ በሚገባ ማመስገን አለብን። [4]ስለዚህ በደረሰባችሁ ስደትና መከራ ሁሉ በመጽናታችሁ፣ እኛ ራሳችን ስለ ትዕግሥታችሁና ስለ እምነታችሁ በእግዚአብሔር አብያተ ክርስቲያናት ዘንድ እንመካለን።

[5]ይህ ሁሉ የእግዚአብሔር ፍርድ ቅን መሆኑን የሚያመለክት ነው፤ ከዚህም የተነሣ መከራን ለምትቀበሉለት ለእግዚአብሔር መንግሥት የበቃችሁ ሆናችሁ ትቈጠራላችሁ። [6]እግዚአብሔር ጻድቅ በመሆኑ መከራን ለሚያመጡባችሁ መከራን ይከፍላቸዋል፤ [7]መከራን ለተቀበላችሁት ለእናንተም ሆነ ለእኛ ደግሞ ዕረፍት ይሰጠናል። ይህም የሚሆነው ጌታ ኢየሱስ በሚንበለበል እሳት ከኀያላን መላእክት ጋር ከሰማይ በሚገለጥበት ጊዜ ነው።

[8]በዚያ ጊዜ እግዚአብሔርን የማያውቁትንና ለጌታችንም ለኢየሱስ ወንጌል የማይታዘዙትን ይበቀላል። [9]እነርሱም ከጌታ ፊትና ከኀይሉ ክብር ተወግደው በዘላለም ጥፋት ይቀጣሉ፤ [10]የሚቀጡትም በቅዱሳኑ ዘንድ ሊከብርና በሚያምኑበትም ሁሉ ዘንድ ሊገረም በሚመጣበት በዚያን ቀን ይሆናል፤ እናንተም ከሚያምኑት መካከል ናችሁ፤ ምስክርነታችንን ተቀብላችኋልና።

[11]ይህን እያሰብን አምላካችን ለጥሪው የበቃችሁ አድርጎ እንዲቈጥራችሁ፣ መልካም ለማድረግ ያላችሁን ምኞትና ከእምነት የሆነውን ሥራችሁን ሁሉ በኀይሉ እንዲፈጽምላችሁ ዘወትር ስለ እናንተ እንጸልያለን። [12]ደግሞም እንደ አምላካችንና[b] እንደ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ መጠን የጌታችን የኢየሱስ ስም በእናንተ ዘንድ እንዲከብርና እናንተም በእርሱ እንድትከብሩ ይህን እንጸልያለን።

## የዐመፅ ሰው

**2** ወንድሞች ሆይ፤ ስለ ጌታችን ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ መምጣትና ወደ እርሱም ስለ መሰብሰባችን ይህን እንለምናችኋለን፤

[a] 1 ግሪኩ *ሲሉያኖስ ይላል*
[b] 12 *ወይም እንደ አምላካችን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ*

1፥1 ሐሥ15፥22፤ 16፥1፤17፥1፤ 1ተሰ1፥1
1፥2 ሮሜ1፥7
1፥3 ሮሜ1፥8፤ ኤፌ5፥20፤1ተሰ3፥12
1፥4 2ቆሮ7፥14፤ 1ተሰ1፥3፡6፤2፥14፤ 3፥3
1፥5 ሉቃ20፥35፤ ፊል1፥28
1፥6 ሉቃ18፥7፡8፤ ሮሜ12፥19፤ ቈላ3፥25፤ራእ6፥10
1፥7 ሉቃ17፥30፤ ዕብ10፥27፤12፥29፤ 2ጴጥ3፥7፤ይሁ14፤ ራእ1፥14
1፥8 መዝ79፥6፤ ኢሳ66፥15፤ ኤር10፥25፤ ሮሜ2፥8፤2ቆሮ2፥12፤ ገላ4፥8
1፥9 2ነገ17፥18፤ ኢሳ2፥10፡19፤ ፊል3፥19፤1ተሰ5፥3፤ 2ተሰ2፥8፤2ጴጥ3፥7
1፥10 ዮሐ17፥10፤ 1ቆሮ1፥6፤3፥13
1፥11 ቀ5፤ ሮሜ1፥10፤8፥28፤ 15፥14፤1ተሰ1፥3
1፥12 ኢሳ24፥15፤ ፊል2፥9-11
2፥1 ማር13፥27፤

1፥1-2፤ የ1ተሰ 1፥1 ማብ ይመ።

1፥3 ወንድሞች፤ የ1ተሰ 1፥4 ማብ ይመ። *እምነታችሁ... ፍቅራችሁም፤* እነዚህ ጳውሎስ የተሰሎንቄ ቤተ ክርስቲያን ምእመናን እንዲኖሯቸው የሚፈልገው ሁለት መልካም ምግባራት ናቸው (1ተሰ 3፥6-7 ይመ)፤ ይጐድሏቸውም የነበሩት እነዚሁ ናቸው (1ተሰ 3፥10፡12)። *እየጨመረ፤* ጳውሎስ ፍቅራቸው እንዲያድግ ሲጸልይ ከተጠቀመበት ግሥ ጋር አንድ ዐይነት ነው (1ተሰ 3፥12)። ቃሉን በዚህ ስፍራ መጠቀሙ፣ ጸሎቱ እንደ ደረሰለት መረዳቱን የሚያሳይ ነው። *አለብን፤* አስፈላጊ በሆነ ጊዜ ሁሉ ጳውሎስ ምስጋናውን ያቀርባል (ከ1ተሰ 1፥7-8 ጋር ያነጻጽሩ፤ የፊል 1፥3-4 ማብ ይመ)።

1፥4 *ስደትና መከራ፤* 1ተሰ 1፥6፤ 2፥14፤ 3፥3 ይመ። *እኛ፤* "ራሳችን" ለሚለው አጽንዖትን ያሳያል። ምንም እንኳ አንዳንድ የቤተ ክርስቲያን መሪዎች ስለ ሥራቸው በትምክህት ቢናገሩም፣ ይህ ያልተለመደ መሆኑን ጳውሎስ ይናገራል (ከ1ተሰ 1፥9 ጋር ያነጻጽሩ)። ሆኖም የተሰሎንቄ ቤተ ክርስቲያን መሪዎች በቅናት ሥራቸውን ይፈጽሙ ስለ ነበር ጳውሎስ በትምክህት እንዲናገር ምክንያት ሆኖታል።

1፥5 *የእግዚአብሔር ፍርድ ቅን መሆኑን የሚያመለክት፤* የተሰሎንቄ ክርስቲያኖች በመከራ ውስጥ በነበራቸው ጽናት የታየ ነው። በእነርሱ ላይ የነበረው ፍርድ ትክክል ነበር፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር ራሳቸው እንዲወጡት አልተዋቸውም። ይጸኑ ዘንድ ኀይልን ሰጥቶአቸዋል፤ ይህም መንፈሳዊና ግብረገባዊ ባሕርይ እንዲያገኙ ረድቶአቸዋል። በተጨማሪም እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር መሆኑንና ለአሳዳጆቻቸውም ማስጠንቀቂያ መስጠቱን ያረጋግጣል (ከፊል1፥28 ጋር ያነጻጽሩ)። *ለምትቀበሉለት፤* "ስለዚያ ነገር ስትሉ" እንደ ማለት ነው። *ለእግዚአብሔር መንግሥት፤* የ1ተሰ2፥12፤ ማቴ 3፥2ማብ ይመ)።

1፥6 *እግዚአብሔር ጻድቅ በመሆኑ ፤* የእግዚአብሔር ጽድቅ ንስሓ በማይገቡ ኀጢአተኞች ላይ ቅጣትን ያስከትላል (ከማር 9፥47-48፤ሉቃ13፥3-5 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይህም ፍርድ አሁን በምድር ላይ (ሮሜ1፥24፡26፡28 ይመ) ወይም በፍርድ ቀን ሊሆን ይችላል።

1፥7 *ለእኛ፤* ጳውሎስ ከርቀት ሆኖ የሚያጽናና ደብዳቤ የሚጽፍ የትምህርት መለኮት ሊቅ ሳይሆን፣ እነርሱ መከራ እንደ ተቀበሉ ሁሉ እርሱም መከራ የሚቀበል ሰው ነበር። *ዕረፍት ይሰጠናል፤* ለእያ ንዳንዱ የሚከፈለው ዋጋ፣ ለክፉ ሰው የሚሰጠውን ቅጣት ብቻ ሳይሆን ለጻድቁ የሚሰጠውንም ዕረፍት ያካትታል። *በሚንበለበል እሳት፤* እርሱ በክፉት ላይ ለመፍረድ እንደሚመጣ ያሳያል (ከኢሳ 66፥15፤ ራእ1፥14 ጋር ያነጻጽሩ)። *ከኀያላን መላእክት፤* የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለመፈጸም ልዩ የሆነ ኀይል የተሰጣቸውን መላእክት ሊያሳይ ይችላል። *በሚገለጥበት ጊዜ፤* ክርስቶስ አሁን ግልጥ ሆኖ አይታይም፤ ብዙዎቹም የእርሱን ሕልውና ይክዳሉ። ተመልሶ ሲመጣ ግን ማን እንደ ሆነ ሁሉ ሰው ያየዋል።

1፥8 *እግዚአብሔርን የማያውቁትን፤* ስለ እውነተኛው አምላክ ፈጽሞ ሰምተው የማያውቁትን ሳይሆን፣ እርሱን አንቀበልም ያሉትን ያመለክታል (ከ2፥10፡12፤ ሮሜ1፥28 ጋር ያነጻጽሩ)። *የማይታዘዙትን፤* ወንጌል እንድንቀበለው ይጋብዘናል፤ ወንጌልን አለ መቀበል ግን ከነገሥታት ንጉሥ የተላለፈውን ትእዛዝ አለመታዘዝ ነው።

1፥9 *ጥፋት፤* ብን ብሎ መጥፋትን አያመለክትም (የ1ተሰ 5፥3 ማብ ይመ)። ጳውሎስ ይህንን ቃል በ1ቆሮ 5፥5 ላይ የተጠቀመው ለድነት ሲባል፣ "የሥጋን" ጥፋት ለማመልከት ነው፤ ድነት የሥጋንም ትንሣኤ ስለሚያካትት፣ "ጥፋት" የሚለው ቃል አገባብ ብትንትን ብሎ መውደምን አያመለክትም። በዚህ ስፍራ ከክርስቶስ ፊት መወገድ ማለት ነው። ይህ ዘላለማዊ የሆነ መለየት፣ ለኀጢአት ተገቢ ቅጣት እና ወደ ገሃነም ለመውረድም መንሥኤ ነው።

1፥10 *በቅዱሳኑ፤* የተሰ3፥13 ማብ ይመ። *በቅዱሳኑ ዘንድ ሊከብር፤* በእርነሱ "መካከል" ብቻ ሳይሆን በእነርሱ "ውስጥ" ማለት ነው፤ የእርሱ ክብር በእነርሱ ማንነት ውስጥ ይታያል። *ሊከብር... በሚመጣበት፤* ይህ ክፍል ክርስቲያኖች ክርስቶስን በአየር ለመቀበል የሚነጠቁበትን ጊዜ ሳይሆን (ዮሐ14፥2-3፤ 1ተሰ4፥17)፣ ኢየሱስ ክርስቶስ በኀይልና በታላቅ ክብር የዚህን ዓለም ሥርዐት ለማጥፋትና የእርሱን የሺህ ዓመት መንግሥት ለመመሥረት የሚመጣበትን ጊዜ ያሳያል (ራእ19፥11-20፥4)። *በዚያ ቀን፤* የ1ተሰ5፥2 ማብ ይመ። *ምስክርነታችንን፤* ወንጌልን መስበክ ማለት እግዚአብሔር በክርስቶስ የሠራውን ሥራ መመስከር ማለት ነው።

1፥11 *መልካም ለማድረግ፤* ለእግዚአብሔር በእምነት የሚደረገውን ማንኛውንም በጎ ዐላማና ተግባር ያበረታታል፤ ጳውሎስም በዚህ ዐይነት ምእመናን ወደ ሙላት እንዲደርሱ ይጸልያል። *ዘወትር...እንጸልያለን፤* የ1ተሰ 5፥17 ማብ ይመ።

1፥12 *ስም፤* በቀድሞ ዘመን የአንድ ሰው ስም፣ ያንን ሰው የሚያመለክት ብቻ ሳይሆን ማንነቱንም የሚናገር ነበር። ጳውሎስ በተሰሎንቄ ክርስቲያኖች ሕይወት ውስጥ በሚሠራው ሥራ ሁሉ ክብሩ ለክርስቶስ እንዲሆን ይፈልጋል።

2፥1 *መምጣት፤* የ1ተሰ2፥19 ማብ ይመ። የክርስቶስ ዳግም ምጽአት የሁለተኛ ተሰሎንቄ መሪ ሐሳብ ነው። የዚህ መልእክት ዐላማ አንዳንድ የሐሰት መምህራን የጌታ ቀን እንደ መጣና የእግዚአብሔር

[2]በመንፈስ መገለጥ ወይም በቃል ወይም ከእኛ እንደተላከ መልእክት የጌታ ቀን ደርሶአል ብላችሁ ፈጥናችሁ ከአእምሮ አችሁ አትናወጡ፤ አትደንግጡም። [3]ማንም ሰው በምንም መንገድ አያታላችሁ፤ አስቀ ድሞ ዐመፅ ሳይነሣ፣ ለጥፋት የተመደበውም የዐመፅ[ሀ] ሰው ሳይገለጥ ያ ቀን አይመጣምና። [4]እርሱም አምላክ ከተባለና ከሚመለከው ነገር ሁሉ በላይ ራሱን ከፍ ከፍ የሚያደርግ ተቃዋሚ ነው፤ እርሱም በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ተቀምጦ፣ "እኔ አምላክ ነኝ" እያለ ዐዋጅ ያስነግራል።

[5]ከእናንተ ጋር በነበርሁበት ጊዜ እነዚ ህን ነገሮች ነግሬአችሁ እንደ ነበር ትዝ አይላችሁምን? [6]በራሱ ጊዜ ይገለጥ ዘንድ አሁን ምን እንደሚከለክለው ታውቃላችሁ። [7]የዐመፅ ምስጢር አሁንም እንኳ እየሠራ ነውና፤ ነገር ግን ይህ የሚሆነው የሚከ ለክለው ከመንገድ እስኪወገድ ድረስ ብቻ ነው [8]ከዚያም በኋላ ጌታ ኢየሱስ በአፉ እስትንፋስ የሚያስወግደውና በምጽአቱም ክብር ፈጽሞ የሚያጠፋው ዐመፀኛ ይገለ ጣል። [9]የዐመፀኛው አመጣጥ በሰይጣን አሠ ራር ላይ የተመሠረተ ሲሆን፣ ይህም በሐ ሰተኛ ታምራት በምልክቶችና በድንቅ ነገሮች ሁሉ ይሆናል፤ [10]እንዲሁም ይድኑ ዘንድ እውነትን ባለመውደድ የሚጠፉትን ሰዎች በሚያታልል በተለያየ የክፋት ሥራ ይመጣል። [11]በዚህም ምክንያት እግዚአብሔር በሐሰት እን ዲያምኑ የስሕተትን አሠራር ይልክባቸዋል፤ [12]ይህም የሚሆነው እውነትን ያላመኑት ነገር ግን በክፋት ደስ ይላቸው የነበሩ ሁሉ እንዲፈረድባቸው ነው።

1ተሰ2፥19፤4፥15-17
2፥2ቍ15፤1ቆሮ1፥8
፤2ተሰ3፥17፤
2ጢሞ2፥18
2፥3ቍ8፤ዳን7፥25፤
8፥25፤11፥36፤
ማቴ24፥10-12፤
ማር13፥5፤
ራእ13፥5፡6
2፥4ኢሳ14፥13፡ 14፤
ሕዝ28፥2፤1ቆሮ8፥5
2፥5 1ተሰ3፥4
2፥6ቍ7
2፥7ቍ6
2፥8ቍ3፤ኢሳ11፥4፤
ሉቃ17፥30፤
ራእ2፥16፤19፥15
2፥9ማቴ4፥10፤
24፥24፤ዮሐ4፥48፤
ራእ13፥13
2፥10ምሳ4፥6፤
ዮሐ3፥17-
19፤1ቆሮ1፥18
2፥11ሮሜ1፥25-28፤
ማቴ24፥5፤ማር13፥5
2፥12ሮሜ1፥32፤
2፥8 2፥13ሮሜ1፥8፤
ኤፌ1፥4፤
1ተሰ5፥9፤1ጴጥ1፥2

## ጸንታችሁ ቁሙ

[13]በጌታ የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ፤ እኛ ግን ሁልጊዜ ስለ እናንተ እግዚአብሔርን ልናመሰግን ይገባናል። ምክንያቱም እግዚአብሔር እናንተን ከመጀመሪያ አንሥቶ በመንፈስ ተቀድሳችሁና በእውነትም አምናችሁ እንድ ትድኑ መርጦአችኋል[ለ] ።

[ሀ]3 አንዳንድ ቅጆች የኀጢአት ይላሉ
[ለ]13 አንዳንድ ቅጆች እግዚአብሔር በኵራት እንድትሆኑ መርጦአ ችኋል ይላሉ

የመጨረሻ ፍርድ እንደ ጀመረ የሚያስተምሩትን ትምህርት ለመቃወም ነው። ጳውሎስ የጻፈው በቃል ላስተማረውና በፊተኛው መልእክቱ ለጻፋቸው ትእዛዞች ተጨማሪ እንዲሆን ነው። *ወደ እርሱም ስለ መሰባሰባችን፤* የ1ተሰ4፥17 ማብ ይመ።

2፥2 *በመንፈስ መገለጥ፤* ማንኛውንም የመንፈስን መገለጥ ያመለክታል። *በቃል፤* ስብከትን ወይም ሌላ የቃል ንግግርን ሊያ መለክት ይችላል። *ከእኛ እንደተላከ መልእክት፤* በማስመሰል የተጻፈ መልእክት ማለት ነው። *እንደ ተላከ፤* የክርስቶስ መም ጣት እውነት ቢሆንም፣ የመጨረሻው ቀናት ጀምረዋል፤ ፍጻሜ ያቸውም አሁን ነው የሚለውን ሐሳብ ጳውሎስ ይቃወማል። *የጌታ ቀን፤* የ1ተሰ5፥2 ማብ ይመ። *አትናወጡ፤* በግሪኩ ቃል አንድ መርከብ ከታሰረበት ቦታ በነፋስ ኀይል ወዲያና ወዲህ መንገላታትንና ጸንቶ መቆም አለመቻልን የሚያመለክት ነው። *አትደ ንግጡም፤* ኢየሱስም ይህን ዐይነት ቃል በመጠቀም ተመሳሳይ ትእዛዝ ሰጥቶአል (ማር 13፥7)።

2፥3 *ዐመፅ፤* በመጨረሻው ጊዜ ብዙዎች ሃይማኖትን ይክዳሉ (ማቴ24፥10-12፤1ጢሞ4፥1 ይመ)። እዚህ ላይ ግን ጳውሎስ የሚናገረው በእግዚአብሔር ሥራ ላይ ፊት ለፊት ስለሚነሣው ዐመፅ ነው። ለጥፋት የተመደበውም ከትዕቢቱ የተነሣ በመጨረሻ መውደቁ የማይቀር ነው፤ ዮሐንስም ስለ አስቆሮቱ ይሁዳ ለመግ ለጽ ተመሳሳይ ቃል ተጠቅሞአል (ዮሐ17፥12 ይመ)። *የዐመፅ ሰው፤* በመጨረሻው ጊዜ ሊመጣ ያለውን የክፉ ኀይላት መሪ የሆነውን ያመለክታል። ይህ ሰው በዚህ ስም የተጠቀሰው በዚህ ቦታ ብቻ ነው። ስለ ብዙ፣ "ሐሰተኛ ክርስቶሶች" ተነግሮአል (1ዮሐ2፥18)፤ ምንም እንኳ ጳውሎስ ስለ ዐመፅ ሰው ዐይነተኛ ባሕርያት ቢገልጽም በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው ግን በራእይ 13 ላይ እንደ ተገለጸው ከሁሉ የከፋው ሳይሆን አቀርም። *ሳይገለጥ፤* ይህ ቃሉ በግሪኩ በ1፥7 ላይ ስለ ክርስቶስ ከሚገልጸው ጋር ተመሳሳይ ስለ ሆነ ከተለመደው የተፈጥሮ ሥርዐት ውጭ የሆነን ነገር ሊያመለክት ይችላል።

2፥4 *አምላክ ከተባለና ከሚመለከው ነገር ሁሉ፤* ይህ የዐመፅ ሰው የፖለቲካ ወይም ወታደራዊ መሪ ብቻ ሳይሆን፣ ከአምልኮ ጋር የተያያዘና ከአማልክት ሁሉ በላይ አድርጎ ራሱን ከፍ ከፍ የሚያደርግ ነው። እንዲያውም አምላክ ነኝ ይላል። *በእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ፤* ሕንጻውን ብቻ የሚያመለክት ነው (ከማር13፥14 ጋር ያነጻጽሩ)፤ በዚያ ውስጥ ሆኖ በእግዚአብሔር ላይ የስድብን ቃል ይናገራል (ከዳን11፥36-45፤ እንዲሁም ከራእ 13፥1-15 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥6 *ምን እንደሚከለክለው፤* ከልካዩ የቀረበው በግዑዝ ጾታ ነው። ነገር ግን በቍጥር 7 ላይ ተባዕት እንደ ሆነ ተገል ጾአል። ስለዚህ ከልካይ ማንነት የተለያዩ አስተያየቶች ተሰን ዝረዋል፦ የሮም መንግሥት ከነገሥታቱ ጋር፤ የጳውሎስ የወንጌል ጕዞ፤ የአይሁድ መንግሥት፤ በመንግሥት አስተዳደር ውስጥ ያለው ሕግ፤ መንፈስ ቅዱስ ወይም መንፈስ ቅዱስ በቤተ ክርስቲያንና በሌሎች የሚሠራው የመከልከል አገልግሎት ናቸው።

2፥7 *ምስጢር፤* ይህ ቃል በአዲስ ኪዳን ብዙውን ጊዜ ሰዎች በራሳቸው ጥረት ማወቅ ያልቻሉትን፣ እግዚአብሔር ብቻ የገለጠላቸውን ነገር ያሳያል (ሮሜ11፥25 ማብ ይመ)። በተጨ ማሪም ወንጌልን ወይም ስለ ወንጌል ያለውን ለማመልከት ጥቅም ላይ ውሎአል፤ ክፍሉ እንደሚያመለክተው ስለ ክፉው የምናውቀው እግዚአብሔር በገለጠልን መጠን ነው። ክፉው አሁንም እየሠራ ነው።

2፥8 *በአፉ እስትንፋስ የሚያስወግደው፤* የዐመፅ ሰው በጣም የሚያስደንቅ ነገር ቢያደርግም እንኳ (ቍ4)፣ ክርስቶስ በቀላሉ ያጠፋዋል (ከዳን11፥45፤ ራእ19፥20 ጋር ያነጻጽሩ)። *ክብር፤* በ2ጢሞ 1፥10 ላይ፣ "መገለጥ" የሚለው የግሪኩ ቃል የክርስቶስን የመጀመሪያ መምጣት ሲያመለክት፣ በቀረው የአዲስ ኪዳን ክፍል ግን ዳግም ምጽአቱን ያመለክታል። *ዐመፀኛ ይገለጣል፤* የመገለጡ ሁኔታ ከተፈጥሮ ውጭ እንደ ሆነ ያሳያል (ቍ9 ይመ)።

2፥9 *አመጣጥ፤* ስለ ክርስቶስ መምጣት በቍ 8 ላይ ከተጠ ቀሰው ቃል ጋር አንድ ነው። ይህን ዐመፀኛ ሰይጣን በታምራት፣ በምልክቶችና በድንቅ ሥራዎች ይሞላዋል (ከማቴ 24፥24 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥10 *እውነትን፤* ብዙ ጊዜ ቃሉ ኢየሱስን (ዮሐ14፥6፤ ኤፌ4፥21 ይመ) ደግሞም ወንጌልን ያመለክታል (ገላ2፥5፤ ኤፌ1፥13 ይመ)። *ባለመ ውደድ፤* አለማመናቸው ሆን ተብሎ ከፈቃዳቸው የመነጨ መሆኑን ያሳያል። *በሚያታልል፤* የቍ 9 ታምራት ዐላ ማ ነው።

2፥11 *በዚህም ምክንያት፤* እያወቁ እውነትን ስለሚቃወሙ ማለት ነው (ቍ 10)። *በሐሰት፤* ተራ ውሸትን ሳይሆን የዐመፅ ሰው አምላክ ነኝ እያለ የሚናገረውን ታላቅ ውሸት ያመለ ክታል። *እግዚአብሔር...የስሕተትን አሠራር ይልክባቸዋል፤* እግዚ አብሔር ኀጢአተኛውን ለመቅጣት ኀጢአትን ይጠቀማል (ከሮሜ 1፥24-28 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥12 *በክፋት ደስ ይላቸው የነበሩ፤* ያወቁትን እውነት ሆን ብሎ መቃወምና እያወቁ በኀጢአት መደሰት በመጨረሻው ቀን በእግዚአብሔር ፍርድ ሥር ለመውደቅ ዐይነተኛ ምክንያት ነው።

2፥13 *በጌታ የተወደዳችሁ...እግዚአብሔር... መርጦአችኋል፤* በእግዚአብሔር ፍቅርና ምርጫ መካከል ስላለው ግንኙነት ቈላ 3፥12፤ 1ተሰ1፥4 ይመ፤ የኤፌ1፥4 ማብ ይመ። *ከመጀመሪያ አንሥቶ፤* ምርጫው ዘላለማዊ ነው (ኤፌ1፥4)። *ተቀድሳችሁ፤* የድነት አንዱ ክፍል እንጂ ለተለዩ ክርስቲያኖች ብቻ የተሰጠ አይደለም (1ተሰ3፥13፤4፥3 እና ማብ ይመ)። *በእውነትም፤* የቍ 10 ማብ ይመ። ሦስቱም የሥላሴ አካላት በዚህ ክፍል ተጠቅሰዋል (የ1ተሰ 1፥1 ማብ ይመ)።

[14]የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ክብር ተካፋዮች እንድትሆኑም በወንጌላችን አማካይነት ጠር ቶአችኋል። [15]እንግዲህ ወንድሞች ሆይ፤ ጸንታችሁ ቁሙ፤ በአንደበታችንም ሆነ በመል እክታችን ያስተላለፍንላችሁን ትምህርት[a] አጥብቃችሁ ያዙ።

[16]ራሱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ደግሞም እኛን የወደደንና በጸጋው የዘላለም መጽና ናትና መልካም ተስፋን የሰጠን እግዚአብሔር አባታችን፣ [17]ልባችሁን ያጽናኑት፤ በበጎ ሥራና በቃል ሁሉ ያበርቷችሁ።

### ለጸሎት የቀረበ ጥያቄ

3 በቀረውስ ወንድሞች ሆይ፤ በእናንተ ዘንድ እንደ ሆነው የጌታ ቃል በፍጥነት እንዲሠራጭና እንዲከበር ለእኛ ጸልዩልን፤ [2]ደግሞም ሰው ሁሉ እምነት ያለው ስለ ማይሆን ከዐመፀኞችና ከክፉ ሰዎች እንድ ንድን ጸልዩልን። [3]ጌታ ግን ታማኝ ነው፤ እርሱም ያበረታችኋል፤ ከክፉውም ይጠብቃ ችኋል። [4]እኛ ያዘዝናችሁን አሁን አደረጋ ችሁ፤ ወደ ፊትም እንደምታደርጉ በጌታ እንታመናለን። [5]ጌታ ልባችሁን ወደ እግዚአ ብሔር ፍቅርና ወደ ክርስቶስ ጽናት ይምራው።

### ሥራ መፍታት እንደማይገባ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

[6]ወንድሞች ሆይ፤ ሥራ ፈት ከሆነና ከእኛ በተቀበላችሁት ትምህርት[b] መሠረት ከማይኖር ወንድም እንድትርቁ በጌታ በኢየሱስ ክርስ ቶስ ስም እናዛችኋለን፤ [7]የእኛን ምሳሌ እን ዴት መከተል እንደሚገባችሁ እናንተ ራሳ ችሁ ታውቃላችሁና። ከእናንተ ጋር በነበ ርንበት ጊዜ ሥራ ፈቶች አልነበርንም፤ [8]ደግ ሞም የማንንም እንጀራ በነጻ አልበላንም፤ ነገር ግን ከእናንተ በአንዳችሁም ላይ ሸክም እንዳንሆን ሌሊትና ቀን እንደክምና እንሠራ ነበር፤ [9]ይህን ያደረግነው ምሳሌነታችንን እንድትከተሉ ብለን እንጂ የሚያስፈልገንን ነገር ከእናንተ ለማግኘት ሥልጣን ሳይኖረን ቀርቶ አይደለም። [10]ከእናንተ ጋር በነበርንበት ጊዜ፣ "ሊሠራ የማይወድ አይብላ" ብለን ይህን ትእዛዝ ሰጥተናችሁ ነበርና።

[11]ከእናንተ አንዳንዶች ሥራ ፈቶች እንደ ሆኑ ሰምተናል፤ እነርሱም ያለ ሥራ እየዞሩ በሰው ጉዳይ ባልቃ የሚገቡ ናቸው። [12]እንደዚህ ያሉ ሰዎች ተግተው ሥራቸውን እንዲሠሩና እንጀራቸውን እንዲበሉ በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም እናዛቸዋለን፤ እንመክራቸዋለ ንም። [13]እናንተ ግን ወንድሞች ሆይ፤ መልካም ሥራን ከመሥራት ከቶ አትታክቱ።

[14]በዚህ መልእክት ላይ ሳለው ቃላችን የማ ይታዘዝ ማንም ቢኖር፣ እንደዚህ ያለውን ሰው በጥንቃቄ ተከታተሉት፤ በሥራውም

2፥14 ሮሜ8፥28፤ 11፥29፤1ተሰ1፥5
2፥15 1ቆሮ11፥2፤ 16፥13
2፥16 ዮሐ3፥16፤ ፊል4፥20
2፥17 1ተሰ3፥2፤ 2ተሰ3፥3
3፥1 1ተሰ1፥8፤2፥13፤ 4፥1፤5፥25
3፥2 ሮሜ15፥31
3፥3 ማቴ5፥37፤ ሮሜ15፥31፤ 1ቆሮ1፥9
3፥4 2ቆሮ2፥3
3፥5 1ዜና29፥18
3፥6 ቊ7፡11፡14፤ ሮሜ16፥17፤ 1ቆሮ5፥4፤11፥2
3፥7 ቊ9፤ 1ቆሮ4፥16
3፥8 ሐሥ18፥3፤ ኤፌ4፥28
3፥9 ቊ7፤1ቆሮ9፥4-14፤16
3፥10 1ተሰ3፥4፤ 4፥11
3፥11 ቊ6፡7፤ 1ጢሞ5፥13
3፥12 ኤፌ4፥28፤ 1ተሰ4፥1፡11
3፥13 ገላ6፥9
3፥14 ቊ6፤ ሮሜ16፥17፤ 1ቆሮ4፥14

[a]15 ወይም ወግ
[b]6 ወይም ወግ

2፥14 *የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ክብር፤* ከ1ተሰ 2፥12 ጋር ያነጻጽሩ። ከእግዚአብሔር ክብር የሚበልጥ ሌላ ክብር የለም። *በወንጌላችን፤* የ1ተሰ1፥5 ማብ ይመ። *በወንጌላችን አማካ ይነት ጠርቶአችኋል፤* በኀላፊ ጊዜ መጻፉ የተሰሎንቄ ክርስ ቲያኖች የዳኑበትን ጊዜ ለማሳየት ነው፤ ነገር ግን በ1ተሰ2፥12፤ 5፥24 ላይ መለኮታዊ ጥሪ የአሁን ጊዜ እውነታ እንደ ሆነ ተመል ክቶአል።

2፥15 *ትምህርት፤* በቁሙ፣ "ትውፊት" ማለት ነው። የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ከመጻፋቸው በፊት መሠረታዊው የክርስትና አስተምህሮ የሙሴ የሕግ መምህራን ያደርጉ እንደ ነበረው በትውፊት ይተላለፍ ነበር (የማቴ15፥2 ማብ ይመ)፤ ይህም በቃል ወይም በጽሑፍ ሊሆን ይችላል። በ1ቆሮ15፥3 ላይ ጳውሎስ ትውፊትንና ባህልን ስለ መቀበልና ስለ ማስተላለፍ የሚገልጹትን ቃላት ተጠቅሞአል።

*2፥16-17፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ጸሎት በመጀ መሪያው መልእክት ውስጥ ይገኛል (1ተሰ 3፥11-13)።

2፥17 *ያጽናኑት ...ያበርቷችሁ፤* እነዚህ ቃላት በ1ተሰ 3፥2 ላይ በአንድነት ተጠቅሰዋል። ጸሎቱ ውስጣዊ ሰውነትን አበርትቶ በቃልና በተግባር ውጤት የሚያስገኝ ነው።

3፥1 *በቀረውስ፤* የ1ተሰ 4፥1 ማብ ይመ። በ1ተሰ5፥25 ላይ ጳውሎስ እንዲ ጸልዩ ይመክራቸዋል፤ እዚህ ላይ ግን በታወቀ ነገር ላይ እንዲጸልዩ ይጋብዛቸዋል። *በእናንተ ዘንድ እንደ ሆነው፤* ይህ አባባል ያለፈውንም ሆነ የአሁኑን የሚያቅፍ አጠ ቃላይ ሐሳብ ነው (ከ1ተሰ2፥13 ጋር ያነጻጽሩ)። *ጸልዩልን፤* ጳውሎስ የክርስ ቶስን ሥራ ለመሥራት የቅዱሳን የጸሎት ድጋፍ አስፈላጊው እንደ ነበር ያመለክታል (ከሮሜ15፥30-32፤ 2ቆሮ1፥11፤ ፊል1፥19፤ ቈላ4፥2፤ 1ተሰ5፥25 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥2 *ዐመፀኞች፤* ግሪኩ፣ "ተገቢውን ስፍራ የለቀቀ" ማለት ሲሆን፣ ሐሳቡ በአዲስ ኪዳን ውስጥ በሌላ ቦታ ተገልጾአል (ሉቃ 23፥41፤ ሐሥ 25፥5)። ጳውሎስ ይህን መልእክት በጻፈበት በቆሮንቶስ ስለ ደረሰበት ችግር ሐሥ 18፥12-13 ይመ።

3፥3 *ታማኝ፤* በግሪኩ "እምነት" (ቊ 2) የሚለውን ቃል ተከትሎ የሚሄድ ሲሆን፣ የእግዚአብሔርን ታማኝነትና የሰዎችን አለመታመን በንጽጽር ያቀርባል (ከ1ቆሮ1፥9፤10፥13፤ 2ቆሮ 1፥18 ጋር ያነጻጽሩ)። *ከክፉውም ይጠብቃችኋል፤* አማኞች በትጋት ሲጸልዩ እግዚአብሔር ከሰይጣን እንደሚጠብቃቸው እርግጠኞች ይሆናሉ፤ እግዚአብሔር ማንኛውንም ዐይነት ፈተና እንዲቋቋሙ ብርታትን ይሰጣቸዋል (1ቆሮ10፥13፤ዕብ2፥18)፤ ከክፉ የአጋንንት ኀይላትም ይጠብቃቸዋል (ኤፌ 6፥12 እና ማብ ይመ)።

3፥5 *ልባችሁን፤* የ1ተሰ 2፥4 ማብ ይመ። *ወደ እግዚአብሔር ፍቅር፤* ጳውሎስ ሥራ ፈትነትን ለመገሠጽ ቢፈልግም እዚህ ላይ ግን ስለ እግዚአብሔር ፍቅር ያሳስባቸዋል። ስለ እግዚአብሔር ፍቅር ብለው ሁሉን የተው ሰዎች ሊያዝኑ አይገባቸውም። *ወደ ክርስቶስ ጽናት፤* የክርስቶስን ዳግም ምጽአት መጠባበቅን ወይም ክርስቶስ በዚህ ምድር ሳለ የነበረውን የጽናት አርአያነትን ሊያ መለክት ይችላል።

3፥6 *ትምህርት፤* የ2፥15 ማብ ይመ። *ሥራ ፈት፤* ይህ ችግር በመጀመሪያው መልእክት ተጠቅሶአል (4፥11-12፤5፥14 እና ማብ ይመ)፤ አሁን ግን እየከፋ ሄደ። ጳውሎስም በዚህ መልእክቱ ከሌላ ነገር ይልቅ ስለዚህ ጉዳይና ስለ ዳግም ምጽአቱ በአጽንዖት ጽፎአል። *እንድትርቁ፤* ያለውን ግንኙነት ሙሉ በሙሉ ማቋረጥን ሳይሆን፣ የጠበቀ ኅብረት እንዳይኖር የሚያሳይ ነው። ሥራ ፈትነት ኀጢአት ነው፤ ሥርዐትንም ያበላሻል፤ ይሁን እንጂ በዚህ ጉዳይ የሚከሰሱ ሰዎች አሁንም በጌታ ወንድሞች እንደ ሆኑ ያሳያል (ቊ15)። ስም፤ የ1፥12 ማብ ይመ። *እናዛችኋለን፤* ወታደራዊ የሆነ የሥልጣን ቃል ነው ።

3፥7 *የእኛን ምሳሌ...መከተል፤* የ1ተሰ 1፥6 ማብ ይመ።

3፥8 *እንጀራ...አልበላንም፤* በዕብራዊ ዘይቤ "ኑሮ መመ ሥረት" እንደ ማለት ነው (ለምሳሌ፣ ዘፍ3፥19፤ አሞ7፥12 ይመ)። ጳውሎስ የሌሎችን ሰዎች መስተንግዶ አለመቀበሉን ሳይሆን፣ ኑሮውን ለመምራት በሌሎች ሰዎች ላይ ጥገኛ አለመሆኑን ያመ ለክታል (1ተሰ2፥9 እና ማብ ይመ)።

3፥9 *ሥልጣን፤* የ1ተሰ 2፥6 ማብ ይመ።

*3፥10፤* አረማውያን "የማይሠራ አይበላም" የሚል ተመሳሳይ አባባል አላቸው፤ ጳውሎስ የሰጠው ግን፣ ትእዛዛዊ ነው፤ "አይብላ" ብሏል። ክርስቲያኖች ሥራ ፈቶች ሊሆኑ አይገባቸውም።

3፥11 *በሰው ጉዳይ ባልቃ የሚገቡ፤* ይህ ሥራ ከመፍታት እጅግ የከፋ ሲሆን በሌሎች ጉዳይ በመግባት ችግር መፍጠርን ያመለክታል፤ ይህም የሥራ ፈትነት ውጤት ነው።

*3፥14፤* ጳውሎስ፣ አንዳንድ ሰዎች ለመልእክቱ ቦታ እንዳ ማይሰጡ ተገንዝቦአል። *አትተባበሩ፤* የግሪኩ ቃል ትርጉም "በአንድ ላይ መደባለቅ" የሚል ሐሳብ ያለው ሲሆን፣ ቃሉ በአዲስ ኪዳን ውስጥ በሌላ ቦታ በ1ቆሮ 5፥9፡11 ላይ ብቻ እንደዚህ ካለው ኅብረት ስለ መለየት ለመግለጽ ተጠቅሶአል። ይህ ቃል

እንዲያፍር ከእርሱ ጋር አትተባበሩ። [15]ሆኖም እንደ ወንድም ገሥጹት እንጂ እንደ ጠላት አትቍጠሩት።

**የመጨረሻ ሰላምታ**

[16]የሰላም ጌታ ራሱ በሁሉም ነገር ዘወትር ሰላም ይስጣችሁ። ጌታ ከሁላችሁ ጋር ይሁን።

3፥15 ገላ6፥1፤ 1ተሰ5፥14፤ፊል16
3፥16 ሩት2፥4፤ ሮሜ15፥33
3፥17 1ቆሮ16፥21
3፥18 ሮሜ16፥20

[17]ይህንን ሰላምታ በገዛ እጄ የጻፍሁት እኔ ጳውሎስ ነኝ፤ የመልእክቶቼም ሁሉ መለያ ይህ ነው፤ አጻጻፌም እንደዚህ ነው።

[18]የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ከሁላችሁ ጋር ይሁን።

ሰውን ወደ ትክክለኛ መስመር ለመመለስ ሲባል የሚደረገውን መለየት ያሳያል።

*3፥15፣* ቤተ ክርስቲያን መውሰድ ያለባት የሥነ ሥርዐት ርምጃ ፍቅርን ያማከለ እንጂ ጭካኔ የተሞላ ሊሆን አይገባም። *ገሥጹት፤* በ1ተሰ 5፥12 ላይ የግሪኩ ትርጕም "አስጠንቅቁት" ማለት ነው።

3፥16 *የሰላም ጌታ፤* የተለመደው ሐረግ "የሰላም አምላክ" የሚለው ነው (የ1ተሰ 5፥23 ማብ ይመ)። *ከሁላችሁ ጋር፤* በሥርዐት የማይመላለሱትንም ይጨምራል

*3፥17፣* ጳውሎስ ብዙ ጊዜ መልእክቱን በቃል እየተናገረ በሰው ያስጽፍ ነበር (ከሮሜ 16፥22 ጋር ያነጻጽሩ)፤ በመጨረሻ ግን በገዛ እጁ አንዳንድ ነገሮችን ጨምሮ ይጽፋል (1ቆሮ 16፥21፤ ገላ 6፥11፤ ቈላ 4፥18 ይመ)። የጳውሎስም ጽሑፍ ከሌሎቹ የሚለየው በዚህ ነው።

*3፥18፣* የ1ተሰ 5፥28 ማብ ይመ። ጳውሎስ ተቃዋሚዎቹን ቢነቅፍም የመጨረሻ ጸሎቱ ግን ለሁሉም ነው።

# መልክታተ ምጋቤ

1ጢሞቴዎስ፣ 2ጢሞቴዎስና የቲቶ መልእክት "መልእክታተ ምጋቤ" በመባል ይታወቃሉ፤ ይህ ስም የተሰጣቸው ጢሞቴዎስና ቲቶ ቤተ ክርስቲያንን እንዴት መጠበቅና መከባከብ እንዳለባቸው መመሪያ ስለሚሰጡ ነው። ሦስቱም መልእክቶች የተጻፉት ምናልባት በሐዋርያት ሥራ 28 ላይ የተወሱት ሁናቶች ከተከናወኑ ታሪካዊ ሁኔታዎች በኋላ ብዙም ሳይቆይ ነው።

ጳውሎስ በሮም ታስሮ ከተፈታ በኋላ (60-23 ዓ.ም ገደማ)፣ አራተኛውን የወንጌል ተልእኮ ጉዞ ሳይጀምር አልቀረም። በዚህ ጉዞው ቲቶ ወኪሉ ሆኖ በቀርጤስ እንዲቈይ፣ ጢ. ሞ ቴዎስ ደግሞ የኤፌሶንን ቤተ ክርስቲያን እንዲጠብቅ አዟቸው ነበር። ከዚያም ጳውሎስ በሰሜን ግሪክ (መቄዶንያ) ወደምትገኘው ወደ ፊልጵስዩስ ተሻገረ፤ በዚያ ሆኖ ለጢሞቴዎስ የመጀመሪያውን መልእክት ሲጽፍ፣ ለቲቶም እንዲሁ (ከ63-65 ዓ.ም ገደማ) ጻፈ። በኋላም ወደ ሮም ሲሄድ ለሁለተኛ ጊዜ ታሰረ፣ ለጢሞቴዎስ ሁለተኛውን መልእክት የጻፈለት ከመገደሉ ከጥቂት ጊዜ በፊት ነው፤ ይህም በ67 ወይም በ68 ዓ.ም መሆኑ ነው።

በመልእክታተ ምጋቤ ውስጥ አንዳንድ መሪ ሐሳቦችና ሐረጎች እየተደጋገሙ ይታያሉ፤ እነርሱም:-
(1) አዳኛችን እግዚአብሔር (የቲቶ 1÷3 ማብ ይመ)፤ (2) ጤናማ ትምህርት፣ እምነትና ማስተማር (የቲቶ 1÷9 ማብ ይመ) (3) እውነተኛ መንፈሳዊነት (የ1 ጢሞ 2÷2 ማብ ይመ) (4) ክርክሮች (1ጢሞ 1÷4፤ 2ጢሞ 2÷23፤ ቲቶ 3÷9) (5) እውነተኛና ሰው ሁሉ ሊቀበለው የሚገባ ቃል ናቸው (የ1ጢሞ 1÷15 ማብ ይመ)።

# የሐዋርያው ጳውሎስ መልእክት
# ወደ ጢሞቴዎስ – አንደኛ

## መግቢያ

### ጸሓፊው

የቤተ ክርስቲያን ትውፊትና መልእክታተ ምጋቢ መግቢያዎች ላይ የሰፈሩት ስላምታዎች፣ መልእክቶቹን የጻፈው ጳውሎስ መሆኑን ያረጋግጣሉ:: ከቅርብ ዓመታት ወዲህ በዚህ መልእክት ውስጥ በሚገኙ የተለዩ ባሕርያት ባላቸው አንዳንድ ቃላትና የአጻጻፍ ስልቶች (የ1፥15፤ 2፥2 ማብ ይመ) መሠረት መልእክታቱ በጳውሎስ ለመጻፉ ያሉት ማስረጃዎች የመልእክቱ ጸሓፊ ጳውሎስ መሆኑን የሚደግፉ ናቸው::

### ታሪካዊ ጻራውና ዐላማው

ጳውሎስ በአራተኛው ሐዋርያዊ ጒዞው ወቅት ወደ መቄዶንያ በመጓዝ ላይ ሳለ (መልእክታተ ምጋቢን ይመ) ጢሞቴዎስ በእስያ ያለችውን ቤተ ክርስቲያን እንዲንከባከባት ትእዛዝ ሰጠው (1፥3):: ሐዋ ርያው በቅርብ ወደ ኤፌሶን መመለስ እንደማይችል በተረዳ ጊዜ (3፥14-15) ጢሞቴዎስ (3፥3:18) ቀደም ሲል ተሰጥቶት በነበረው ኀላፊነት በተጨማሪ በወቅቱ ተከስቶ የነበረውን ኑፋቄ በትክክለኛው ትምህርት እንዲከላከል አዘዘው (2፥3-7፤ 4፥1-8፤ 6፥3-5:20-21):: በማደግ ላይ ያለችውን የኤፌሶንን ቤተ ክርስቲያን ልዩ ልዩ ጒዳዮች በበላይነት እንዲቈጣጣር (የአምልኮ ሥርዐቱን 2፥1-15፤ ተገቢ አገልጋዮችን እንዲሾም 3፥1-13፤ 5፥17-25) ይህን የመጀመሪያ መልእክት ጻፈለት::

በኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን የነበረው ትልቁ ችግር የኖስትሳውያን ትምህርት (የ1ኛ ዮሐንስ መግቢያ ይመ)፣ እያሽቈለቈለ ያለው የይሁዲ ሃይማኖት (1፥3-7) እና ብሕትውናን (4፥1-5) ቀላቅሎ የያዘ የሐ ሰት ትምህርት ነው::

### የተጻፈበት ጊዜ

1ኛ ጢሞቴዎስ የተጻፈው በግምት ከ63-65 ዓ.ም. ባለው ጊዜና በሐሥ 28 ላይ የተዘገበው ታሪክ ከተፈጸመ በኋላ ነበር:: ይኸውም ጳውሎስ በኤፌሶን ለሦስት ዓመት አገልግሎት ከነበረበት ጊዜ ከስምንት ዓመት በኋላ ነበር (ሐሥ 19፥8:10፤ 20፥31)::

### የመልእክቱ ተደራሲ

ሰላምታው እንደሚያመለክተው (1፥2) ጳውሎስ ደብዳቤውን የጻፈው የልስትራን ተወላጅ ለሆነው ለጢሞቴዎስ ነው:: ልስትራን በዛሬዋ ቱርክ ውስጥ የምትገኝ ከተማ ናት:: የጢሞቴዎስ አባት ግሪካዊ፣ ሲሆን፣ እናቱ ይሁዲ (ሐሥ 16፥1) ነበረች:: ጢሞቴዎስ ከልጅነቱ ጀምሮ የብሉይ ኪዳን ትምህርት ተምሮአል (2ጢሞ 1፥5፤ 3፥15):: ጳውሎስ ወደ ልስትራን ባደረገው የመጀመሪያ ጒዞው ጢሞቴዎስን ወደ ጌታ በማምጣቱ "በእምነት እውነተኛ ልጅ" (1፥2) ይለዋል፤ ጳውሎስ በሁለተኛው የልስትራን ጒብኝቱ ጢሞቴዎስ ከእርሱ ጋር እንዲሆንና በወንጌል ጒዞው እንዲተባበረው ይጠራዋል:: ጢሞቴዎስ በአባቱ ግሪካዊ በመሆኑ ይህ ሁኔታ በአይሁድ መካከል በሚሠሩት የወንጌል ሥራ ላይ ዕንቅፋት እንዳይሆንበት ጳውሎስ ጢሞቴዎስን ገረዘው (ሐሥ 16፥3):: ጢሞቴዎስ በመቄዶንያና በአካያ በነበረው የወንጌል አገልግሎት (ሐሥ 17፥14-15፤ 18፥5) ውስጥ ተሳትፎ አድርጎአል:: ጳውሎስ በኤፌሶን ረጃጅም ስብከቶችን በሰጠበት የአገልግሎት ጊዜያት (ሐሥ 19፥22) ከእርሱ ጋር ነበር:: በተጨማሪም ከኤፌሶን ወደ መቄዶንያና ወደ ቆሮንቶስ፣ ከዚያ ተመልሶም ወደ መቄዶንያና ወደ ትንሹ እስያ (ሐሥ 20፥1-6) ከጳውሎስ ጋር ተጒዞአል:: እስከ ኢየሩሳሌም እንኳ ሳይቀር ከእርሱ ጋር የሄደ ይመስላል:: ጳውሎስ ለመጀመሪያ ጊዜ ሲታሰርም አብሮት ነበር (ፊል 1፥1፤ ቈላ 1፥1፤ ፊሞ 1):: ጳውሎስ በሐሥ 28 የተጻፈው ታሪክ ከተፈጸመ በኋላ ከእስራት ተፈትቶ አራተኛውን የወንጌል ጒዞውን ሲያደረግ ከእርሱ ጋር ተጒዞአል:: በመጨረሻ ግን ጳውሎስ ወደ መቄዶንያ ሲሄድ ጢሞቴዎስ በኤፌሶን በተከሰተው የኑፋቄ ትምህርት ምክንያት በዚያ ቈየ:: ጳውሎስ ከጢሞቴዎስ ጋር የነበረው መቀራረብና ለጢሞቴዎስ የነበረው መልካም ግምት ከጻፋቸው መልእክቶች መካከል ስድስቱን ከጢሞቴዎስ ጋር ሆኖ በመላኩና በመልእክቶቹም ላይ ስሙን መጥቀሱ (2ኛ ቆሮንቶስ፣ ፊልጵስዩስ፣ ቈላስይስ፣ 1ኛና 2ኛ ተሰሎንቄ እና ፊልሞና) እንዲሁም ለፊልጵስዩስ ሰዎች ስለ ጢሞቴዎስ በጎ ምስክርነት በመስጠት አድናቆቱን ገልጾአል :: ጳውሎስ በሕይወቱ መጨረሻ ጢሞቴዎስ ወደ እርሱ ወደ ሮም እንዲመጣ ጠይቆት ነበር (2ጢሞ 4፥19:21):: ጢሞቴዎስ ራሱ ታስሮ እንደ ነበረና ወዲያኑ እንደ ተለቀቀ በዕብ 13፥23 ላይ ተገልጾአል፤ ነገር ግን የታሰረው በሮም ወይም በሌላ ስፍራ መሆኑ በትክክል አልታወቀም::

ጢሞቴዎስ ሐዋርያ አልነበረም፤ ኤጲስ ቆጶሳት የሚሾሙበት መመሪያ ስለተሰጠውም (3፥1-7፤ 5፥17-22) ምናልባት ኤጲስ ቆጶስም ላይሆን ይችላል:: ስለዚህ ልዩ ሥራ ይሠራ ዘንድ (ቲቶ 1፥5 ይመ) ሐዋርያዊ ውክልና የተሰጠውና የተላከ አገልጋይ ተደርጎ ቢቈጠር ተገቢ ነው::

**አስተዋፅኦ**

1. ሰላምታ (1፥1-2)
2. ስለ ሐሰት አስተማሪዎች የተሰጠ ማስጠንቀቂያ (1፥3-11)
   ሀ. የኑፋቄው ልዩ ባሕርይ (1፥3-7)
   ለ. ሕግ ዐላማ (1፥8-11)
3. ለጳውሎስ የተሰጠው የጌታ ጸጋ (1፥8-11)
4. ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ መመሪያ የሰጠበት ዐላማ (1፥18-20)
5. ስለ ቤተ ክርስቲያን አስተዳደር የተሰጠ መመሪያ (ም 2-3)
   ሀ. የጉባኤ አምልኮ (ም 2)
      (1) በጉባኤ አምልኮ ጸሎት (2፥1-8)
      (2) ሴቶች በጉባኤ አምልኮ (2፥9-15)
   ለ. ስለቤተ ክርስቲያን መሪዎች ብቃት መመዘኛ (3፥1-13)
      (1) ለኤጲስ ቆጶሳት (3፥1-7)
      (2) ለዲያቆናት (3፥8-13)
   ሐ. የእነዚህ መመሪያዎች ዐላማ (3፥14-16)
6. የሐሰት ትምህርትን የመከላከያ ዘዴ (ም 4)
   ሀ. የሐሰት ትምህርት ምንነት (4፥1-5)
   ለ. የሐሰት ትምህርት እንዴት መከላከል እንደሚቻል (4፥6-16)
7. ምእመናንን በተለያየ ደረጃ የማስተዳደር ዘዴ (5፥1-6፥2)
   ሀ. ሽማግሌዎችንና ወጣቶችን (5፥1-2)
   ለ. መበለቶችን (5፥3-16)
   ሐ. የቤተ ክርስቲያን ሽማግሌዎችን (5፥17-25)
   መ. ባሪያዎችን (6፥1-2)
8. ልዩ ልዩ ጉዳዮች (6፥3-19)
   ሀ. የሐሰት መምህራን (6፥3-5)
   ለ. ፍቅረ ንዋይ (6፥6-10)
   ሐ. ለጢሞቴዎስ የተሰጠ ትእዛዝ (6፥11-16)
   መ. ባለጠጎች (6፥17-19)
9. ማጠቃለያ (6፥20-21)

1 በአዳኛችን በእግዚአብሔር፣ ተስፋችንም በሆነው በክርስቶስ ኢየሱስ ትእዛዝ የክርስቶስ ኢየሱስ ሐዋርያ ከሆነው ከጳውሎስ፤

[2]በእምነት እውነተኛ ልጄ ለሆነው ለጢሞቴዎስ፤

ከእግዚአብሔር ከአባታችን፣ ከጌታችንም ከክርስቶስ ኢየሱስ ጸጋና ምሕረት፣ ሰላምም ይሁን።

## ከሐሰተኛ የሕግ መምህራን ስለ መጠበቅ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

[3]ወደ መቄዶንያ በሄድሁ ጊዜ ዐደራ እንዳልሁህ፣ አንዳንድ ሰዎች ከእንግዲህ የሐሰት ትምህርት እንዳያስተምሩ ታዛቸው ዘንድ በዚያው በኤፌሶን ተቀመጥ፤ [4]ደግሞም ለተረትና መጨረሻ ለሌለው የትውልዶች ታሪክ ራሳቸውን አሳልፈው እንዳይሰጡ እዘዛቸው። እነዚህ ነገሮች በእምነት ከሆነው ከእግዚአብሔር ሥራ ይልቅ ክርክርን ያነሣሣሉ። [5]የዚህ ትእዛዝ ዐላማ ግን ከንጹሕ ልብ፣ ከበጎ ኅሊና እንዲሁም ከእውነተኛ እምነት የሚገኝ ፍቅር ነው። [6]አንዳንዶች ከእነዚህ ነገሮች ዘወር ብለው ወደ ከንቱ ንግግር ተመልሰዋል። [7]የሕግ መምህራን ለመሆን ይፈልጋሉ፤ ሆኖም ስለሚናገሩት ወይም አስረግጠው ስለሚያገቱለት ነገር አያውቁም።

[8]ነገር ግን ሰው በአግባቡ ከተጠቀመበት፣ ሕግ መልካም መሆኑን እናውቃለን። [9]ደግሞም ሕግ[ሀ] የተሰጠው ለጻድቃን ሳይሆን፣ ለሕግ ተላላፊዎችና ለዐመፀኞች፣ ፈሪሃ እግዚአብሔር ለሌላቸውና ለኀጢአተኞች፣ ቅድስና ለሌላቸውና እግዚአብሔርን ለሚንቁ፣ አባትና እናታቸውን ለሚገድሉ፣ ለነፍስ ገዳዮች መሆኑን እናውቃለን፤ [10]እንዲሁም ለዘማውያን፣ ከወንድ ጋር ለሚተኙ ወንዶች፣ ሰውን ለሚሸጡና ለሚገዙ፣ ለውሸተኞች፣ በሐሰት ለሚምሉ፣ ጤናማ የሆነውን ትምህርት ለሚጻረሩ ሁሉ ነው፤ [11]ይህ ጤናማ ትምህርት ብሩክ እግዚአብሔር ለእኔ በዐደራ ከሰጠኝ የክብር ወንጌል ጋር የሚስማማ ነው።

## ለጳውሎስ የተሰጠው የጌታ ጸጋ

[12]በአገልግሎቱ በመሾም ታማኝ አድርጎ የቈጠረኝን፣ ብርታት የሰጠኝን ጌታችንን ክርስቶስ ኢየሱስን አመሰግናለሁ። [13]ምንም እንኳ ከዚህ በፊት ተሳዳቢ፣ አሳዳጅና ዐመፀኛ የነበርሁ ብሆንም፣ ባለማወቅና ባለማመን ስላደረግሁት ምሕረት ተደርጎልኛል፤ [14]በክርስቶስ ኢየሱስ ከሆኑት እምነትና ፍቅር ጋርም የጌታችን ጸጋ ተትረፈረፈልኝ።

[15]‘ክርስቶስ ኢየሱስ ኀጢአተኞችን ለማዳን ወደ ዓለም መጣ’ የሚለው ቃል እውነተኛና ሰው ሁሉ ሊቀበለው የሚገባ ነው፤ ከኀጢአተኞችም ዋና እኔ ነኝ። [16]ነገር ግን ክርስቶስ ኢየሱስ በእርሱ ለሚያምኑና የዘላለምን ሕይወት ለሚቀበሉ ወሰን የሌለው ትዕግሥቱን ከኀጢአተኞች ዋና በሆንሁት በእኔ እንደ ምሳሌ አድርጎ ያሳይ ዘንድ ምሕረትን አገኘሁ። [17]እንግዲህ ዘላለማዊ ለሆነው፣ ለማይሞተው፣ ለማይታየውና ብቻውን አምላክ ለሆነው ንጉሥ ከዘላለም እስከ ዘላለም ክብርና ምስጋና ይሁን፤ አሜን።

[18]ልጄ ጢሞቴዎስ ሆይ፤ አስቀድሞ ስለ አንተ በተነገረው ትንቢት መሠረት ይህን

[ሀ]9 ወይም ሕጉ

1፥1 ሉቃ 1፥47፤ 2ቆሮ 1፥1፤ ቈላ 1፥27፤ ቲቶ 1፥3
1፥2 ቍ 18፤ ሐሥ 16፥1፤ ሮሜ 1፥7፤ 1ቆሮ 4፥17፤ 1ተሰ 2፥11፤ 2ጢሞ 1፥2፤ ቲቶ 1፥4
1፥3 ሐሥ 16፥9፤ 18፥19፤ ገላ 1፥6:7፤ 1ጢሞ 6፥3
1፥4 1ጢሞ 4፥7፤ 2ጢሞ 2፥14፤ 4፥4፤ ቲቶ 1፥14፤ 3፥9
1፥5 ሐሥ 23፥1፤ ገላ 5፥6፤ 1ጢሞ 4፥2፤ 2ጢሞ 1፥5፤ 2፥22
1፥7 ኢዮ 38፥2፤ ኤፌ 4፥11
1፥8 ሮሜ 7፥12
1፥9 ገላ 3፥19፤ 5፥23
1፥10 1ጢሞ 6፥3፤ 2ጢሞ 1፥13፤ 4፥3፤ ቲቶ 1፥9፤ 2፥1
1፥11 ገላ 2፥7፤ 1ተሰ 2፥4፤ ቲቶ 1፥3
1፥12 ሐሥ 9፥15፤ ፊል 4፥13
1፥13 ቍ 16፤ ሐሥ 8፥3፤ 26፥9
1፥14 2ቆሮ 4፥15፤ 1ተሰ 1፥3፤ 2ጢሞ 1፥13
1፥15 ማር 2፥17፤ ዮሐ 3፥17፤ 1ጢሞ 3፥1፤ 4፥9፤ 2ጢሞ 2፥11፤ ቲቶ 3፥8
1፥16 ቍ 13፤ ማቴ 25፥46፤ ዮሐ 3፥15፤ ሮሜ 2፥4
1፥17 ሮሜ 11፥36፤ ቈላ 1፥15፤ 1ጢሞ 6፥16፤ ይሁ 25፤ ራእ 15፥3
1፥18 ቍ 2፤ 1ጢሞ 4፥14፤ 6፥12፤ 2ጢሞ 2፥3፤ 4፥7

1፥1 *ተስፋችን በሆነው በክርስቶስ ኢየሱስ፣* ቲቶ 2፥13 ይመ። *ተስፋችን፣* ምኞትን ብቻ ሳይሆን ፍጹም እርግጠኝነትን የሚገልጽ ነው። *ሐዋርያ፣* በልዩ ሁኔታ በራሱ በክርስቶስ የተሾመ (የማር 6፥30፤ 1ቆሮ 1፥1፤ ዕብ 3፥1 ማብ ይመ)።

1፥2 *በእምነት እውነተኛ ልጄ፣* መንፈሳዊ ልጄ ማለት ነው (1፥18፤ 1ቆሮ 4፥17፤ 2ጢሞ 1፥2፤ 2፥1፤ ፊሞ 10 ይመ)። *ጸጋ፣* የዮና 4፥2 ገላ 1፥3፤ ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ። *ምሕረት፣* ሮም 9፥23፤ ማብ ይመ። *ሰላም፣* የዮሐ 14፥27፤ 20፥19፤ የገላ 1፥3 ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ ።

*1፥3-11፣* ጳውሎስ በዚህ ክፍልና በ4፥1-8፤ 6፥3-5:20-21 ላይ የኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን ከመናፍቃን አስተማሪዎች መጠበቅ እንደሚገባት ያስገነዝባል። መናፍቃኑም የሚታወቁባቸው ዐይነተኛ መለያዎች፡- (1) የሐሰት ትምህርቶችን ማስተማራቸው (1፥3፤ 6፥3)፣ (2) የአይሁድን ከንቱ ተረት ማስተማራቸው (ቲቶ 1፥14)፣ (3) የብሉይ ኪዳንም ሕግ መምህራን ለመሆን መፈለጋቸው (1፥7)፣ (4) ባልታወቀው የትውልዶች ቈጠራ ላይ የተመሠረቱ መጨረሻ የሌላቸውንና የተጋነኑትን የሐሰት ታሪኮች ማስፋፋታቸው (1፥4፤ 4፥7፤ ቲቶ 3፥9)፣ (5) ራሳቸውን ከፍ አድርገው መመልከታቸው (1፥7፤6 4)፣ (6) ክርክር መውደዳቸው (1፥4፤ 6፥4፤ 2ጢሞ 2፥23፤ ቲቶ 3፥9)፣ (7) ከንቱና (1፥6) የማይረባ ነገር መናገራቸው (2ጢሞ 2፥23፤ ቲቶ 3፥9)፣ (8) የሚናገሩትን ነገር አለማወቃቸው (1፥7፤ 6፥4)፣ (9) የብሕትውናን ልምምዶችን ማስተማራቸው (4፥3)፣ (10) የመንፈሳዊ መሪነት ሥልጣናቸውን የግል መጠቀሚያ ያደርጋሉ (6፥5)። ምናልባት እነዚህ መናፍቃን የኖስትሳውያን ትምህርት መንገድ ጠራጊዎች ሳይሆኑ አይቀሩም (6፥20-21 ፣ ከ1ዮሐ መግቢያ ላይ ስለ ኖስትሳውያን የተጻፈውን ይመ)።

1፥3 *ወደ መቄዶኒያ በሄድሁ ጊዜ፣* ይህ ታሪክ በሐዋርያት ሥራ መጽሐፍ ያልተጻፈበት ምክንያት፣ ምናልባት ታሪኩ ከሐዋ 28 በኋላ ጳውሎስ በሮም ለመጀመሪያና ለሁለተኛ ጊዜ በታሰረባቸው ጊዜያት መካከል የተፈጸመ በመሆኑ ሊሆን ይችላል (መግቢያውን ይመ)። *በኤፌሶን ተቀመጥ፣* በዚህ ጊዜ የኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን ሥር እየሰደደች ነው፤ ጳውሎስም ከስምንት ዓመት በፊት በሦስተኛው የወንጌል ጕዞው ወቅት፣ በዚህች አገር ሰፊ የአገግሎት ሥራ አከናውኖ ነበር (ሐሥ 19፥1-20፥1)፤ ከሮም እስር ቤት ከተለቀቀ በኋላም (ከሐሥ 28 በኋላ) ቤተ ክርስቲያኒቱን እንደ ገና ከጎበኘና ጢሞቴዎስን ኀላፊ አድርጎ ከሾመ በኋላ ወደ መቄዶኒያ ዐለፈ።

1፥4 *ለተረትና መጨረሻ ለሌለው የትውልዶች ታሪክ* ምናልባትም በብሉይ ኪዳን የትውልዶች ቈጠራ ታሪክ ላይ የተመሠረቱና በኋላ ግን ወደ ተወሳሰበ የኖስትሳውያን ፍልስፍና ትምህርት ያደጉ ተረታ ተረቶች ሊሆኑ ይችላሉ (ከ1ኛ ዮሐንስ መግቢያ “ኖስትሳውያን ትምህርት” የሚለውን ይመ)።

1፥8 *ሕግ መልካም መሆኑን፣* ሮም 7፥7-12 ይመ።

1፥10 *ጤናማ የሆነውን ትምህርት፤* ቲቶ 1፥9 ማብ ይመ።

1፥11 *በዐደራ ከሰጠኝ፤* 6፥20፤ 1ቆሮ 9፥17፤ ገላ 2፥7፤ 1ተሰ 2፥4፤ 2ጢሞ 1፥12:14፤ 2፥2 ይመ። *ወንጌል፣* የማር 1፥1 ማብ ይመ።

1፥13 *ተሳዳቢ ፣አሳዳጅና ዐመፀኛ የነበርሁ፣* ሐሥ 9፥1፤ 22፥4-5:19፤ 26፥10-11 ይመ።

1፥15 *የሚለው ቃል እውነተኛ፣* ይህ ዐይነቱ አባባል በመልእክታተ ምጋቤ ውስጥ ቍልፍ ሐረግ ሆኖ አምስት ጊዜ ከመጠቀሱ በስተቀር፣ በየትኛውም የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ አይገኝም (3፥1፤ 4፥9፤ 2ጢሞ 2፥11፤ ቲቶ 3፥8)።

1፥18 *አስቀድሞ ስለ አንተ በተነገረው ትንቢት መሠረት፣* በጥንት ቤተ ክርስቲያን፣ እግዚአብሔር ፈቃዱን በነቢያት በኩል ይገልጽ ነበር (ጳውሎስንና በርናባስን ለወንጌል አገልግሎት ወደ አሕዛብ እንዲላኩ ያደረጉት ነቢያት ነበሩ ሐሥ 13፥1-3 ይመ። ጢሞቴዎስን በተመለከተ ግን ትንቢቱ የተነገረው እርሱ ከተሾመ በኋላ ወይም ከመሾሙ በፊት (4፥14)፣ ምናልባትም ከሐዋርያው ጳውሎስ ሁለተኛው የወንጌል ጕዞ ዐሥራ ሁለት ዓመት

ትእዛዝ እሰጥሃለሁ፤ ይኸውም እርሱን በመከተል መልካሙን ገድል እንድትጋደል ነው። [19]እምነትና በጎ ኅሊናም ይኑርህ፤ አንዳንዶች ኅሊናቸውን ጥለው ባሕር ላይ አደጋ ደርሶበት እንደሚጠፋ መርከብ እምነታቸውን አጥፍተዋል። [20]ከእነርሱም መካከል እንዳይሳደቡ ትምህርት ያገኙ ዘንድ ለሰይጣን አሳልፌ የሰጠኋቸው፣ ሄሜኔዎስና እስክንድሮስ ይገኙበታል።

## አምልኮን በሚመለከት የተሰጠ መመሪያ

**2** እንግዲህ ከሁሉ አስቀድሞ ልመናና ጸሎት፣ ምልጃና ምስጋና ለሰዎች ሁሉ፣ ለነገሥታትና ለባለ ሥልጣናት ሁሉ እንዲደረግ አሳስባለሁ፤ [2]ይህም በእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወትና በቅድስና ሁሉ፣ በሰላምና በጸጥታ እንድንኖር ነው። [3]ይህ በእግዚአብሔር በአዳኛችን ፊት ደስ የሚያሰኝ ነው፤ [4]እርሱ ሰዎች ሁሉ እንዲድኑና እውነትን ወደ ማወቅ እንዲደርሱ ይፈልጋል። [5]አንድ እግዚአብሔር አለና፤ ደግሞም በእግዚአብሔርና በሰዎች መካከል አንድ አስታራቂ አለ፤ እርሱም ሰው የሆነው ክርስቶስ ኢየሱስ ነው፤ [6]ራሱንም ለሰዎች ሁሉ ቤዛ አድርጎ ሰጠ፤ ይህም በትክክለኛው ጊዜ ተመስክሮለታል። [7]እኔም ለዚህ ነገር የምሥራች አብሣሪና ሐዋርያ እንዲሁም ለአሕዛብ የእውነተኛ እምነት አስተማሪ ሆኜ ተሾምሁ፤ እውነቱን እናገራለሁ፤ አልዋሽም።

[8]እንግዲህ ወንዶች በሁሉም ቦታ ያለ ቍጣና ያለ ክርክር የተቀደሱ እጆቻቸውን ወደ ላይ በማንሣት እንዲጸልዩ እፈልጋለሁ።

[9]እንዲሁም ሴቶች በጨዋነትና ራስን በመግዛት ተገቢ የሆነ ልብስ ይልበሱ እንጂ በሹሩባ ወይም በዕንቁ ወይም ዋጋቸው ውድ በሆኑ ልብሶች አይሸቀርቀሩ፤ [10]ነገር ግን እግዚአብሔርን እናመልካለን የሚሉ ሴቶች ሊያደርጉ እንደሚገባ በመልካም ተግባር ይዋቡ።

[11]ሴት በጸጥታና በሙሉ መገዛት ትማር። [12]ሴት ዝም እንድትል እንጂ እንድታስተምር ወይም በወንድ ላይ ሥልጣን እንዲኖራት አልፈቅድም። [13]ምክንያቱም አዳም ቀድሞ ተፈጥሮአል፤ ከዚያም ሔዋን ተፈጠረች። [14]ደግሞም የተታለለው አዳም አይደለም፤ የተታለለችውና ኃጢአተኛ የሆነችው ሴቷ ናት፤

1፥19 ቊ5፤ሐሥ23፥1፤ 1ጢሞ6፥21፤ 2ጢሞ2፥18
1፥20 1ቆሮ5፥5፤ 2ጢሞ2፥17፤ 2ጢሞ4፥14
2፥1 ኤፌ6፥18
2፥2 ዕዝ6፥10፤ ሮሜ13፥1፤ 1ጢሞ3፥16፤4፥7፡8፤6፥3፡5፡6፡11፤ 2ጢሞ3፥5፤ቲቶ1፥1
2፥3 ሉቃ1፥47፤ 1ጢሞ5፥4
2፥4 ሕዝ18፥23፡32፤33፥11፤ዮሐ3፥17፤ ሮሜ11፥14፤ 1ጢሞ4፥10፤2ጢሞ2፥25 ቲቶ1፥1፤2፥11፤ ዕብ10፥26፤2ጴጥ3፥9
2፥5 ዘዳ6፥4፤ ሮሜ1፥3፤3፥29፡30፤10፥12፤ ገላ3፥20
2፥6 ማቴ20፥28፤ 1ቆሮ1፥6፤1ጢሞ6፥15፤ ቲቶ1፥3
2፥7 ሐሥ9፥15፤ ሮሜ9፥1፤2ጢሞ1፥11
2፥8 መዝ24፥4፤63፥4፤134፥2፤141፥2፤ ሉቃ24፥50
2፥9 1ጴጥ3፥3
2፥10 ምሳ31፥13
2፥11 1ጴጥ3፥3፡42፥12 ኤፌ5፥22
2፥13 ዘፍ2፥7፡ 22፤ 1ቆሮ11፥8 2፥14 ዘፍ3፥1-6፡13፤ 2ቆሮ11፥3

---

ቀደም ብሎ ሊሆን ይችላል (ሐሥ 16፥3 ይመ)። ምናልባት ትንቢቱ ጢሞቴዎስ በቤተ ክርስቲያን አመራር ውስጥ ስላለው ታላቅ ሚና የሚገልጽ ሊሆን ይችላል።

1፥20 *ለሰይጣን አሳልፌ የሰጠኋቸው፤* ቤተ ክርስቲያን አባሎቿን የምትቀጣበትን የሥነ ሥርዐት ቅጣት የሚያመለክት ነው (የማቴ 18፥17 ማብ ይመ)። ጳውሎስ እነዚህን ሁለት ሰዎች ከሰይጣን ፍላጻ መከላከያ ከሆነችው ቤተ ክርስቲያን አስወገዳቸው። እንዳይሳደቡ ይማሩ ዘንድ ከማኅበረ ምእመናን አንድነትና ከቤተ ክርስቲያን እንክብካቤ መለየቱ ተገቢ ነው። ተመሳሳይ ለሆነ ሁኔታ 1ቆሮ 5፥5፡13 እንዲሁም የ1ቆሮ 5፥5 ማብ ይመ። ከክርስቶስ አካል ጋር ማለትም ከቤተ ክርስቲያን ጋር መተባበር፣ ከሰይጣን ኀይል ይጠብቀናል፤ በሌላ በኩል ደግሞ ከቤተ ክርስቲያን መባረር ሕይወትን ለጥፋት ይዳርጋል፤ ክፉ ለሆነው የሰይጣን ፈተናም ያጋልጣል። ቤተ ክርስቲያን አባሎቿን የምትቀጣበት ምክንያት ተቀጪውን ወደ እውነተኛ ንስሓ፣ ወደ ትክክለኛ መሠረተ እምነትና በክርስቶስ ወደሚገኘው ድነት ለማምጣት ነው (1ቆሮ 5፥5 እና ማብ ይመ)። *ሄሜኔዎስ፤* 2ጢሞ 2፥17-18 ይመ። *እስክንድሮስ፤* በ2ጢሞ 4፥14 ላይ የተጠቀሰው እስክንድሮስ ሊሆን ይችላል (ያንኑ ማብ ይመ)።

2፥1 *ለነገሥታትና ስለ ባለ ሥልጣናት ሁሉ፤* ኤር 29፥7 ይመ። ጳውሎስ ይህን መልእክት በሚጽፍበት ጊዜ ኔሮ(54-68 ዓ.ም.) የተባለው የሮማውያን ቄሳር በሥልጣን ላይ ነበረ።

2፥2 *በእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት፤* በመልእክታተ ምጋቤ ውስጥ ይህ ቍልፍ ሐረግ ነው፤ በ1ጢሞቴዎስ ውስጥ ስምንት ጊዜ (3፥16፤ 4፥7-8፤ 6፥3፡5-6፡11)፤ በ2ኛ ጢሞቴዎስ ውስጥ አንድ ጊዜ (3፥5)፤ እንዲሁም በቲቶ ውስጥ አንዴ (1፥1) ተጠቅሶአል፤ ነገር ግን በተቀሩት የጳውሎስ መልእክታት ውስጥ ይህ ሐረግ አይገኝም። ሐረጉ መልካምንና የተቀደሰን ሕይወት የሚያሳይ፣ ለምንጨውም ልዩ ትኵረት የሚሰጥና ለእግዚአብሔርም ታላቅ አክብሮት እንደሚገባው የሚያመለክት ነው።

2፥4 *እርሱ ሰዎች ሁሉ እንዲድኑ…ይፈልጋል፤* የእግዚአብሔር ፍላጎት ሰዎች ሁሉ እንዲድኑ ነው። የሰዎችን ድነት በተመለከተ እግዚአብሔር እንዲድኑ (ለዘላለም ሕይወት) የመረጣቸው ሁሉንም ሰዎች ሳይሆን ጥቂቶችን ብቻ ነው የሚሉ አሉ (ለምሳሌ 1ጴጥ 1፥2)። ሌሎች ደግሞ እንዲህ ዐይነቱን ምንባብ የሚረዱት እግዚአብሔር የመረጣቸው የወንጌልን ቃል እንደሚያምኑ አስቀድሞ ስለሚያውቅ ነው ይላሉ። ሌሎች ተርጓሚዎች ደግሞ እንደዚህ ያሉትን እርስ በርሳቸው የማይጣጣሙ መስለው የሚታዩትን ነገሮች፣ የሰው አእምሮ አጥጋቢ ምክንያት ሰጥቶ ለማስታረቅ ባይችልም መጽሐፍ ቅዱስ ሁለቱንም እውነታዎች ስለሚያስተምር የሚቃረኑ መሠረተ ሐሳቦች አይደሉም ባዩች ናቸው። ያም ሆነ ይህ እግዚአብሔር የሚድኑትን ሰዎች ያውቃል (የሮም 8፥29 ማብ ይመ)።

2፥5 *አንድ እግዚአብሔር አለ፤* ይህ የአይሁድ ሃይማኖት መሠረተ እምነት ነው (ዘዳ 6፥4)፤ እያንዳንዱም አይሁድ በጸሎቱ ጊዜ በየቀኑ ይህንኑ ያስታውቃል (የማር 12፥28 ማብ ይመ)።

2፥6 *ቤዛ፤* የማቴ 20፥28 ማብ ይመ። *በትክክለኛው ጊዜ፤* የገላ 4፥4 ማብ ይመ። *ተመስክሮለታል፤* ክርስቶስ ራሱን ቤዛ አድርጎ የሰጠበትን ሐዋርያዊ ምስክርነት ነው።

2፥7 *ለዚህ ነገር፤* ክርስቶስ በመሞቱ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል የነበረውን የጥል ግድግዳ አፍርሶ ድነትን ለሰው ሁሉ ማዘጋጀቱን ማለቱ ነው። *አብሣሪ፤* በአደባባይ ዐዋጅ እንደሚናገር ባለ ሥልጣን ማለት ነው። *ሐዋርያ፤* የማር 6፥30፤ 1ቆሮ 1፥1 ማብ ይመ።

*2፥8-14፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ ስለ ሴቶች የሰጠው ትምህርት፣ ታሪካዊ ሁኔታ ያለው እንጂ በሁሉ ቦታና ለሁሉ ጊዜ የሚያገለግል አይደለም የሚሉ አሉ። ሌሎች ግን የክፍሉ ትምህርት በአንድ የታሪክ ወቅት ብቻ የሚወሰን ሳይሆን በየትኛውም ዘመን ሊሠራ የሚችል ነው ይላሉ።

2፥8 *ወንዶች፤* በግሪኩ ቃል መሠረት ለወንዶች ብቻ በተለየ ሁኔታ የገባ ነው። በ1ቆሮ 11፥5 ላይ እንደ ተመለከተው ሴቶች በአደባባይ መጸለያቸውን የሚጠቁም ነገር አለ።

*2፥9፤* የተለያዩ ጌጣ ጌጦችን ማድረግንና ጠጕርን ሹሩባ መሠራት መከልከሉ ሳይሆን፣ የቅንጦትንና የትዕቢትን ምልክቶች እንዳይሆኑ ማስጠንቀቂያ መስጠቱ ነው፤ 2፥10፤1ጴጥ 3፥3-4 ይመ።

2፥12 *ሴት…እንድታስተምር…አልፈቅድም፤* አንዳንዶች፣ እዚህ ላይ ጳውሎስ አያስተምሩ ያላቸው ሴቶች፣ በኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን ውስጥ እንደሚገባ ሳይማሩ ለማስተማር የሚሞክሩትን ነው ይላሉ፤ እነዚህ ሴቶች፣ ወንዶችን ለመጨቈን ሥልጣናቸውን ይጠቀማሉ። አንዳንዶች ደግሞ ሴቶች በቤተ ክርስቲያን ውስጥ አስተማሪ ሊሆኑ (ተደርገው ሊሾሙ) አይገባቸውም ማለቱ ነው ይላሉ። ይህም ሴቶች የበላይ ሆነው ወንዶችን ወደ ማስተዳደር እንዳያዘነብሉ ማለትም የቤተ ክርስቲያን እረኛ ሆነው እንዳያገለግሉ በተደረገው እገዳ ላይ ተመልክቶአል (የ3፥1 ማብ ይመ)።

*2፥13-14፤* ጳውሎስ ይህን የከለከለው ዘፍጥረት ም 2-3 መሠረት አድርጎ ነው። አንዳንዶች፣ “ምክንያቱም” የሚለው ቃል የሴትየዋን ዝምታና ራሷን የማስገዛት ኀላፊነቷን የሚያመለክት ሳይሆን፣ ቍጥር 5 ላይ እንደ ተመለከተው ዐረፍተ ነገሮችን ለማያያዝ የገባ ነው ይላሉ። ስለዚህ በዘፍጥረት ውስጥ ቅድሚያ ለአዳም መስጠቱ፣ በኤፌሶን እንዲያስተምሩ ለወንዶች የተሰጠውን ቅድሚያ ያመለክታል፤ እንዲሁም የሔዋን መታለል፣ በኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ካስመማራቸው የተነሣ ወደ ሐሰት ትምህርት የሄዱትን ያመለክታል። ስለዚህ እገዳው ዓለም ዐቀፋዊና ቋሚ ሳይሆን፣ በቤተ ክርስቲያኒቱ ጕዳይ ላይ ብቻ ያተኮረ

15ይሁን እንጂ ሴት[ሀ] በእምነትና በፍቅር፣ በቅድስናም ራሷን እየገዛች ብትጸና ልጅ በመውለድ ትድናለች[ለ]::

## እረኞችና ዲያቆናት

3 “ማንም የቤተ ክርስቲያን ኤጲስ ቆጶስ ለመሆን ቢፈልግ፣ መልካም ሥራን ይመኛል” የሚለው ቃል የታመነ ነው:: 2እንግዲህ የቤተ ክርስቲያን ኤጲስ ቆጶስ የማይነቀፍ፣ የአንዲት ሚስት ባል፣ ልከኛ፣ ራሱን የሚገዛ፣ በሥርዐት የሚኖር፣ እንግዳ ተቀባይ፣ ማስተማር የሚችል፣ 3የማይሰክር፣ የማይጣላ ግን ጨዋ የሆነ፣ የማይጨቃጨቅ፣ ገንዘብንም የማይወድ ሊሆን ይገባዋል:: 4ልጆቹን ታዛዥና አክባሪ አድርጎ በማሳደግ የገዛ ቤተ ሰቡን በአግባቡ የሚያስተዳድር ሊሆን ይገባል:: 5አንድ ሰው የራሱን ቤት ማስተዳደር ካላወቀበት፣ የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን እንዴት ሊጠብቅ ይችላል? 6በትዕቢት ተነፍቶ ዲያብሎስ በወደቀበት ፍርድ እንዳይወድቅ አዲስ ክርስቲያን አይሁን:: 7ደግሞም ስሙ እንዳይነቀፍና በዲያብሎስ ወጥመድ ውስጥ እንዳይወድቅ፣ በውጭ ባሉት ዘንድ መልካም ምስክርነት ሊኖረው ይገባል::

8ዲያቆናትም እንደዚሁ የተከበሩ፣ ቃላቸውን የማይለዋውጡ፣ ለብዙ ወይን ጠጅ የማይጎመጁ፣ ያለ አግባብ የሚገኝ ጥቅምንም የማያሳድዱ ሰዎች መሆን ይገባቸዋል፤ 9የእምነትንም ጥልቅ ምስጢር በንጹሕ ኅሊና መጠበቅ አለባቸው:: 10እነርሱም አስቀድመው ይፈተኑ፤ ከዚያም፣ አንዳች ነቀፋ ካልተገኘባቸው በዲቁና ያገልግሉ::

11እንዲሁ ሴቶችም[ሐ] የተከበሩ፣ ሐሜተኞች ያልሆኑ ነገር ግን ልከኞችና በነገር ሁሉ የታመኑ ሊሆኑ ይገባል::

12ዲያቆናት የአንዲት ሚስት ባል መሆን ይገባቸዋል፤ ደግሞም ልጆቻቸውንና ቤተ ሰቦቻቸውን በአግባቡ የሚያስተዳድሩ መሆን አለባቸው:: 13በአግባቡ ያገለገሉ ለራሳቸው ትልቅ ክብርን፣ በክርስቶስ ኢየሱስም ባላቸው እምነት ብዙ ድፍረትን ያገኛሉ::

14ወደ አንተ ቶሎ ለመምጣት ተስፋ ባደርግም ይህን ትእዛዝ እጽፍልሃለሁ፤ 15ይህንም የምጽፍልህ ብዘገይ እንኳ ሰዎች በእግዚአብሔር ቤት እንዴት መኖር እንዳለባቸው እንድታውቅ ነው፤ ቤቱም የሕያው እግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን ይኸውም የእውነት ዐምድና መሠረት ነው:: 16የእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት ምስጢር ያለ ጥርጥር ታላቅ ነው፤

እርሱ[መ] በሥጋ[ሠ] ተገለጠ፤<br>
በመንፈስ ጸደቀ፤

2፥15 1ጢሞ1፥14<br>
3፥1 ሐሥ20፥28፤ ፊል1፥1፤1ጢሞ1፥15፤ ቲቶ1፥7<br>
3፥2 ቍ11:12፤ ሮሜ12፥13፤ 2ጢሞ2፥24፤ ቲቶ1፥6-8፤2፥2<br>
3፥3 ሉቃ16፥14፤ 1ጢሞ6፥10፤ 2ጢሞ2፥24፤3፥2፤ ቲቶ1፥7፤ዕብ13፥5፤ 1ጴጥ5፥2<br>
3፥4 ቍ12፤ቲቶ1፥6<br>
3፥5 1ቆሮ10፥32<br>
3፥6 1ጢሞ6፥4፤ 2ጢሞ3፥4፤2ጴጥ2፥4<br>
3፥7 ማር4፥11፤ 2ጢሞ2፥26<br>
3፥8 ፊል1፥1፤ 1ጢሞ5፥23፤ ቲቶ1፥7፤2፥3<br>
3፥9 ሐሥ23፥1<br>
3፥10 1ጢሞ5፥22<br>
3፥11 ቍ2፤2ጢሞ3፥3፤ ቲቶ2፥3<br>
3፥12 ቍ2:4<br>
3፥15 ቍ5፤ ማቴ16፥16፤1ቆሮ10፥32<br>
3፥16 መዝ9፥11፤ ማር16፥19፤ ዮሐ1፥14፤ ሮሜ16፥25፤ ቈላ1፥23፤1ጢሞ2፥2

[ሀ]15 ግሪኩ *እርሷ* ይላል [ለ]15 ወይም *ትታደሳለች*<br>
[ሐ]11 ወይም *ሚስቶቻቸው ወይም ዲያቆናውያት*<br>
[መ]16 አንዳንድ ቅጆች *አምላክ* ይላሉ::<br>
[ሠ]16 ወይም *በአካል*

ነው (በመግቢያው ላይ “ታሪካዊ ዳራና ዐላማ” የሚለውን ይመ):: በሌላ ስፍራ ይህ ትእዛዝ ጥቅም ላይ ውሎ አናገኝም (ለምሳሌ 1ቆሮ 11፥1-5):: ሌሎች ደግሞ ዘፍጥረትን መጠቀሙ እገዳውን ዓለም ዐቀፋዊና ዘላቂነት ያለው ቋሚ መልክ እንዲይዝ ያደርገዋል ብለውም ናሉ፤ ለምሳሌ:- (1)አዳም ቀድሞ ተፈጥሮአል፤ አዳም ከውድቀት በፊት በፍጥረት ጊዜ የነበረውን ቅድሚያ ያሳስባል:: በዚህ ምንባብ ውስጥ የተጠቀሰው የሴትና የወንድ ግንኙነት በፍጥረት ታሪክ ላይ የተመሠረተ መሆኑን ያሳያል:: (2) የተታለለችው ሴቷ ናት፤ ሴቲቱ ራሷ ስታ አዳምንም ስለአሳተችው፣ አንድ የቤተ ክርስቲያን እረኛ በአደባባይ ቆሞ የሚሰጠውን የማስተማር አገልግሎት ሴት ታከናውን ዘንድ የታመነች ልትሆን እንደማትችል ይገልጻል ይላሉ::

*2፥15፣* ይህ ጥቅስ የሚከተሉትን ሦስት ትርጒሞች እንደያዘ ይታሰባል፤ እነርሱም:- (1) በቤተ ሰብ ውስጥ በሚስትነትና በእናትነት የተሰጣትን ኀላፊነት በሚገባ ስለምትወጣ እግዚአብሔር ስለምትፈራ ሴት ይናገራል፤ (2) ከሁሉ በሚበልጠው መወለድ ማለትም በሥጋ ከተገለጠው ከክርስቶስ መንፈሳዊ ድነት የሚያገኙትን ሴቶች ይመለከታል፤ (3) ልጅ በሚወልዱበት ወቅት ከማንኛውም አካላዊ ጒዳት የሚጠበቁትን ሴቶች ይመለከታል::

3፥1 *የቤተ ክርስቲያን ኤጲስ ቆጶስ፤* በግሪክ ባህል፣ ሐረጉ የአንድ ማዘጋጃ ቤት ወይም የአንድ የሃይማኖት ክፍል መሪን ያመለክታል:: በዚህ ጥቅስ መሠረት ግን፣ ትርጒሙ የአንድ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን ወይም ማኅበረ ምእመናን ጠባቂ ማለት ነው:: በአይሁድ እምነትና ትምህርት ላይ በተመሠረተው ክርስትና፣ “የቤተ ክርስቲያን እረኛ” እና “ሽማግሌ” ተመሳሳይ ትርጒም አላቸው፤ እነዚህ ቃላት በዐረፍተ ነገር ውስጥ በሐሥ 20፥17:28፤ ቲቶ 1፥5-7፤ 1ጴጥ 5፥1-2 በመለዋወጥ ገብተዋል:: የቤተ ክርስቲያን እረኛ ኀላፊነቶች ማስተማርና መስበክ (3፥2፤ 5፥17)፤ የቤተ ክርስቲያኑን ጒዳይ መምራት (3፥5፤ 5፥17)፤ የእግዚአብሔርን መንጋ በእረኝነት መጠበቅ (ሐሥ20፥28)፤ ቤተ ክርስቲያንን ከሐሰት ትምህርት መጠበቅ (ሐሥ 20፥28-31) ናቸው:: *የሚለው ቃል የታመነ ነው፤* የ1፥15 ማብ ይመ::

3፥2 -3 *የቤተ ክርስቲያን ኤጲስ ቆጶስ... ሊሆን ይገባዋል፤* “የሽማግሌዎችና የዲያቆናት መመዘኛ” የሚለውን ሠንጠረዥ በገጽ 1842 ላይ ይመልከቱ:: *የአንዲት ሚስት ባል፤* ከአንድ በላይ በማግባት ወይም ለትዳር ጓደኛ ታማኝ ባለመሆን እግዚአብሔር የደነገገው የጋብቻ ሕግ እንዳይጣስ የወጣ አጠቃላይ መመሪያ ነው (የቲቶ 1፥6 ማብ ይመ)::

3፥5 *ቤተ ክርስቲያን፤* የማቴ 16፥18 ማብ ይመ::

3፥8 *ዲያቆናት፤* በግሪኩ “የሚያገለግል” ማለት ነው:: በሐሥ 6፥1-6 ላይ የተመረጡት ሰዎች የመጀመሪያዎቹ የአዲስ ኪዳን ዲያቆናት ብቻ ሳይሆኑ፣ ምናልባትም የቤተ ክርስቲያን የመጀመሪያዎቹ ተሿሚዎች ሳይሆኑ አይቀሩም (ያንኑ ማብ ይመ):: በአጠቃላይ አገልግሎታቸው፣ ሽማግሌዎች ሙሉ ጊዜያቸውን ለጸሎትና ለቃሉ አገልግሎት ያውሉ ዘንድ ማኅበራዊ አገልግሎት መስጠት ነው (ሐሥ 6፥2:4):: በአዲስ ኪዳን የተጠቀሱ ሁለቱ የአጥቢያ ቤተ ክርስቲያን የአገልግሎት ሹመቶች የቤተ ክርስቲያን እረኛ (ሽማግሌ) እና ዲያቆን የተባሉት ናቸው (ፊል 1፥1 ይመ)::

3፥11 *ሴቶች፤* በግሪክ ለዚህ ሐረግ የተሰጠው ቃል የሚከተሉትን ሊያመለክት ይችላል፤ (1) የዲያቆናትን ሚስቶች፣ (2) ሴት ዲያቆናት፣ ነገር ግን ወንዶች ዲያቆናት ከቍ 12-13 ላይ በድጋሚ መጠቀሳቸው እዚህ ላይ ለሴት ዲያቆናት የተለየ የአገልግሎት ስፍራ የሌለ ያስመስላል:: ብዙዎች ግን የሚሉት ተቃራኒውን ነው::

3፥12 *የአንዲት ሚስት ባል፤* የቍ 2ን ማብ ይመ::

3፥14 *ይህን ...እጽፍልሃለሁ፤* እዚህ ላይ፣ ጳውሎስ መልእክቱ የተጻፈበት ዋና ዐላማ የቤተ ክርስቲያንን አስተዳደር በተመለከተ ትምህርት መስጠት መሆኑን ባጭሩ ይገልጻል::

3፥16 *የእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት ምስጢር፤* የሮሜ 11፥25፤ የቈላ 1፥26 ማብ ይመ:: ይህ ምስጢር ከታች ባሉት ቃላት እንደ ተመለከተው ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ እንጂ ስለ ሌላ አይደለም:: ክርስቶስ ሥጋ መሆኑ (ሥጋዌ) በሁሉም አቅጣጫ (በተለይም በማዳን ሥራው) ለእውነተኛ መንፈሳዊነት መሠረት ነው:: ምናልባት ቃላቱ በግጥም መልክ መጻፋቸው የጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ሃይማኖቷን ለመግለጽ ከምትጠቀምበት መዝሙር የተወሰደ ሊሆን ይችላል (የቈላ 3፥16 ማብ ይመ):: *በመንፈስ ጸደቀ፤* ኢየሱስ አጋንንትን እንዲያወጣ (ማቴ 12፥28) እንዲሁም ታምራትን እንዲያደርግ መንፈስ ቅዱስ አስቻለው፤ ከሁሉ በላይ ግን መንፈስ ቅዱስ ኢየሱስን ከሞት በማስነሣት (ሮሜ 1፥4፤ 1ጴጥ 3፥18 ይመ) የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑን አረጋገጠ::

# የጳውሎስ አራተኛው የወንጌል ጉዞ

62 - 68 ዓ.ም

ከሐሥ 13:1 - 21:17 ባለው ክፍል እንደሚታየው ጳውሎስ ሦስት የወን ጌል ጉዞዎች እንዳደረገ ግልጽ ነው:: በሐሥ 28 ከተዘገበው ከሮም እስር ቤት በኋላ አራተኛውን የወንጌል ተልእኮ እንዳደረገ መረዳት ይቻላል:: ይህ ጉዞ ተደርጓል የሚለው ድምዳሜ መሠረት ያደረጋቸው ነጥቦች:- (1) ጳውሎስ ወደ እስጳንያ ለመሄድ እንዳሰበ መናገሩ (ሮሜ 15:24-28)፤ (2) ጳውሎስ በሮም ለመጀመሪያ ጊዜ ታስሮ ከተፈታ በኋላ ያለውን ሁኔታ ከሚገልጸው የኢሴቢዮስ ዘገባ (የቤተ ክርስቲያን ታሪክ 2.22 2.3) እና (3) ቀደምት የክርስቲያን ጽሑፎች ወንጌልን እስከ ስፔን (እስጳንያ) ድረስ መውሰዱን መግለጻቸው (የሮማው ቀሌሜንጦስ «ወደ ቆሮንቶስ ሰዎች የተላከ መልእክት» ም 5 እና ሌሎችም) ናቸው::

ጳውሎስ ከእስራቱ በኋላ የጎበኛቸው ቦታዎች የታወቁት ከቀደሙቱ ጽሑፎቹና በመልእክታቱ ምጋቤ ውስጥ ወደ እነዚህ ቦታዎች ለመሄድ እንዳቀደ በመጠቀሳቸው ነው:: የጉዞዎቹ ቅደም ተከተል በእርግጠኝነት አይታወቅም፤ ሆኖም በስተቀኝ በኩል የተመለከተውን የጉዞ ተርታ ተከትሎ ሊሆን ይችላል::




1. ሮም- ከእስር በ 62 ዓ.ም ተፈታ
2. እስጳንያ- 62-64 ዓ.ም (ሮሜ 15:24፤28)
3. ቀርጤስ- 64-65 ዓ.ም (ቲቶ 1:5)
4. ሚሊጢን- 65 ዓ.ም (2ጢሞ 4:20)
5. ቈላስይስ- 66 ዓ.ም (ፊሞ 22)
6. ኤፌሶን- 66 ዓ.ም (1ጢሞ 1:3)
7. ፊልጵስዩስ- 66 ዓ.ም (ፊል 2:23-24፤ 1ጢሞ 1:3)
8. ኒቆጵልዮን- 66-67 ዓ.ም (ቲቶ 3:12)
9. ሮም- 67 ዓ.ም
10. ሰማዕትነት- 67/68 ዓ.ም

በመላእክት ታየ፤
በአሕዛብ ዘንድ ተሰበከ፤
በዓለም ባሉት ታመነ፤
በክብር ዐረገ።

## ለጢሞቴዎስ የተሰጠ መመሪያ

**4** በኋለኞች ዘመናት አንዳንዶች እምነትን ክደው አታላይ መናፍስትንና የአጋንንትን ትምህርት እንደሚከተሉ መንፈስ በግልጥ ይናገራል። [2]እንዲህ ያለው ትምህርት የሚመጣው ኅሊናቸው በጋለ ብረት የተጠበሰ ያህል ከደነዘዘባቸው ግብዝ ውሸተኞች ነው። [3]እነርሱ፣ ሰዎች እንዳያገቡ ይከለክላሉ፤ የሚያምኑና እውነትን የሚያውቁ ሰዎች እግዚአብሔር የፈጠረውን በምስጋናም የሚቀበሉትን እንዳይበሉ ያዛሉ፤ [4]እግዚአብሔር የፈጠረው ማንኛውም ነገር መልካም ነውና፤ በምስጋና ከተቀበሉትም የሚጣል ምንም ነገር የለም፣ [5]በእግዚአብሔር ቃልና በጸሎት የተቀደሰ ነውና።

[6]ይህን ትእዛዝ ለወንድሞች ብታሳስብ፣ በእምነት ቃልና በተቀበልኸው መልካም ትምህርት ታንጸህ የክርስቶስ ኢየሱስ በጎ አገልጋይ ትሆናለህ። [7]እግዚአብሔርን ከማያከብር ርባና ቢስ አፈ ታሪክና ከአሮጊቶች ተረትተረት ራቅ፤ ይልቁንም ለእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት ራስህን አሠልጥን። [8]የአካል ብቃት ልምምድ ለጥቂት ነገር ይጠቅማልና፤ ለእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት ራስን ማሠልጠን ግን ለአሁኑም ሆነ ለሚመጣው ሕይወት ተስፋ ስላለው ለሁለቱም ይጠቅማል።

[9]ይህ ቃል የታመነና ሙሉ ለሙሉ ሊቀበሉት የሚገባ ነው፤ [10]ለዚህ ብለን እንጥራለን፤ እንደክማለንም፤ ይኸውም ለሰዎች

4፥1 ማር13፥5፤ ዮሐ16፥13፤ሐሥ8፥29፤ 1ቆሮ2፥10፤2ጢሞ3፥1፤ 2ጴጥ3፥3
4፥2 ኤፌ4፥19
4፥3 ቈላ4፤ዘፍ1፥29፤ 9፥3፤ሮሜ14፥6፤ 1ቆሮ10፥30፤ ቈላ2፥16፤ዕብ13፥4
4፥4 ዘፍ1፥10፡12፡ 18፡21፡25፡31፤ ማር7፥18፤1፡9፤ ሮሜ14፥14-18፤ ሐሥ10፥15
4፥5 ዕብ4፥12
4፥6 1ጢሞ1፥10፤ 2ጢሞ3፥15
4፥7 1ጢሞ1፥4፤2፥2፤ 2ጢሞ2፥16
4፥8 መዝ37፥9፡11፤ ምሳ22፥4፤ማቴ6፥33፤ ማር10፥29፡30፤ 1ጢሞ6፥6
4፥9 1ጢሞ1፥15 4፥10 ማቴ16፥16፤ ሉቃ1፥47፤2፥11

*በመላእክት ታየ፤* በትንሣኤውና (ማቴ 28፥2) በዕርገቱ ጊዜ (ሐሥ 1፥10) የሆነውን ለመግለጽ ነው።

4፥1 *በኋለኞቹ ዘመናት፤* ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዚህች ምድር ላይ በሥጋ ከተገለጠበት ጊዜ አንሥቶ ያለውን ጊዜ የሚያመለክት ነው (የዕብ 1፥1 ማብ ይመ)። ጳውሎስ ስለ ሐሰት ትምህርቶች የጻፈው፣ ከክርስቶስ ዳግም ምጽአት ጥቂት ቀደም ባለው ጊዜ ብቻ የሚከሰቱ መሆናቸውን በማመልከት ሳይሆን፣ መልእክቱን በጻፈበት ጊዜ እንኳ ማቈጥቈጥ መጀመራቸውን በማመልከት መሆኑን በቍጥር 7 ላይ በግልጽ መረዳት ይቻላል። *መንፈስ በግልጥ ይናገራል፤* ለምሳሌ ማቴ 24፥11፤ ማር 13፥22፤ ሐሥ20፥29-30፤ 2ተሰ 2፥3 ይመ። እዚህ ላይ ግን ጳውሎስ የሚናገረው ከመንፈስ ቅዱስ ስላገኘው ልዩ መገለጥ ሳይሆን አይቀርም።

*4፥3፤* ይህ መጽሐፍ ቅዱሳዊ ያልሆነ፣ ሥጋን የሚጨቍን ትምህርት የመነጨው ለኖስቲሳውን ትምህርት መሠረት ከሆነው ቍስ ርኩስ ነው ከሚለው ትምህርት ነው (ከ1ዮሐንስ መግቢያ፣ "የኖስቲሳውያን ትምህርት" የሚለውን ይመ )።

4፥7 *ከአሮጊቶች ተረትተረት፤* የ1፥4 ማብ ይመ። *ለእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት ራስህን አሠልጥን፤* የ2፥2 ማብ ይመ። እግዚአብሔርን ለማክበር ራስን በሥርዐት መግራትን ይጠይቃል።

4፥9 *ይህ ቃል የታመነ፤* የ1፥15 ማብ ይመ። ይህም በቍ 8 ላይ ያለውን ምሳሌያዊ ንግግር ወደ ኋላ ተመልሶ ያሳያል፤ በቍ 10 ላይ፣ "እንጥራለን፤ እንደክማለን" የሚለው ደግሞ ከቍ 7-8 የተጠቀሰውን ያመለክታል።

4፥10 *ተስፋ፤* የ1፥1 ማብ ይመ። *የሰዎች ሁሉ... አዳኝ በሆነው፤* እግዚአብሔር ሰዎችን ሁሉ ከዘላለም ቅጣት ያድናቸዋል ማለት እንዳልሆነ ግልጽ ነው፤ እያንዳንዱ ሰው ድነት ያገኛል የሚለው ሐሳብ ከቃለ እግዚአብሔር ትምህርት ጋር በቀጥታ የሚቃረን ነው። እግዚአብሔር ወደ እርሱ ለሚመጡት ሰዎች ሁሉ ድነት ስለሚሰጥ አዳኝ ነው።

**የሽማግሌዎችና የዲያቆናት መመዘኛ**

| | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| ራሱን የሚገዛ | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥2፤ቲቶ1፥8 | የማይነቀፍ | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥2፤ቲቶ1፥6<br>1ጢሞ3፥9 |
| እንግዳ ተቀባይ | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥2፤ቲቶ1፥8 | የአንዲት ሚስት ባል | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥2<br>ቲቶ3፥12 |
| ማስተማር የሚችል | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥2፤5፥17፤ቲቶ1፥9 | ልከኛ | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥2፤ቲቶ1፥6<br>1ጢሞ3፥8 |
| የማይጣላ ግን ጨዋ | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥3፤ቲቶ1፥7 | በሥርዐት የሚኖር | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥2<br>1ጢሞ3፥8 |
| የማይጨቃጨቅ | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥3 | የማይሰክር | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥3፤ቲቶ1፥7<br>1ጢሞ3፥8 |
| ገንዘብንም የማይወድ | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥3 | የገዛ ቤተ ሰቡን በአ<br>ግባቡ የሚያስተዳድር | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥4<br>1ጢሞ3፥12 |
| በውጭ ባሉት ዘንድ<br>መልካም ምስክርነት ያለው | ሽማግሌ | 1ጢሞ3፥7 | ታዛዥና አክባሪ<br>ልጆቻቸውን ...<br>የሚያስተዳድሩ | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | 1ጢሞ3፥4-5፤ቲቶ1፥6<br>1ጢሞ3፥12 |
| በራሱ የማይመካ | ሽማግሌ | ቲቶ1፥7 | ተገቢ ባልሆነ መንገድ<br>ለጥቅም የማይሮጥ | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | ቲቶ1፥7<br>1ጢሞ3፥8 |
| ግልፍተኛ ያልሆነ | ሽማግሌ | ቲቶ1፥7 | የእምነትን ጥልቅ<br>ምስጢር በንጹሕ<br>ኅሊና የሚጠብቅ | ሽማግሌ<br>ዲያቆን | ቲቶ1፥9<br>1ጢሞ3፥9 |
| በጎ የሆነውን ነገር<br>የሚወድ | ሽማግሌ | ቲቶ1፥8 | ቃላቸውን የማይለውጡ | ዲያቆን | 1ጢሞ3፥8 |
| ቅን፣ቅዱስ | ሽማግሌ | ቲቶ1፥8 | የተፈተኑ | ዲያቆን | 1ጢሞ3፥10 |
| ራሱን የሚገዛ | ሽማግሌ | ቲቶ1፥8 | | | |

ሁሉ በተለይም ለሚያምኑት አዳኝ በሆነው በሕያው እግዚአብሔር ተስፋ ስለምናደርግ ነው።

[11]እነዚህን ነገሮች እዘዝ፤ አስተምርም። [12]ወጣትነትህን ማንም አይናቅ፤ ነገር ግን ለሚያምኑት በንግግርና በኑሮ፣ በፍቅር፣ በእምነትና በንጽሕና አርአያ ሁንላቸው። [13]እኔ እስክመጣ ድረስ ለማንበብ፣ ለመምከርና ለማስተማር ትጋ። [14]ሽማግሌዎች እጃቸውን በአንተ ላይ ሲጭኑ በትንቢት የተሰጠህን የጸጋ ስጦታ ቸል አትበል።

[15]ሰው ሁሉ ማደግህን ያይ ዘንድ በእነዚህ ነገሮች ላይ አትኵር፤ በትጋትም ፈጽማቸው፤ [16]ለሕይወትህና ለትምህርትህ ተጠንቀቅ፤ በእነዚህም ጽና፤ ይህን ብታደርግ፣ ራስህንና የሚሰሙህንም ታድናለህና።

## ስለ መበለቶች፣ ስለ ሽማግሌዎችና ስለ ባሪያዎች የተሰጠ ምክር

**5** አረጋዊውን ሰው እንደ አባትህ ቈጥረህ ምከረው እንጂ በኀይለ ቃል አትናገረው። ወጣት ወንዶችን እንደ ወንድሞች ተቀበላቸው፤ [2]እንዲሁም አሮጊቶችን እንደ እናቶች፣ ወጣት ሴቶችን ደግሞ እንደ እኅቶች በፍጹም ንጽሕና አስተናግዳቸው።

[3]በእርግጥ ችግረኛ የሆኑትን መበለቶች ተንከባከባቸው። [4]አንዲት መበለት ግን ልጆች ወይም የልጅ ልጆች ቢኖሯት፣ እነዚህ ልጆች የራሳቸውን ቤተ ሰብ በመርዳትና ለወላጆቻቸውም ብድራትን በመመለስ ከሁሉ በፊት እምነታቸውን በተግባር ለማሳየት መማር ይገባቸዋል፤ ይህ እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ ነውና። [5]በእርግጥ መበለት የሆነች፣ ብቻዋን የምትኖር ተስፋዋን በእግዚአብሔር ላይ ታደርጋለች፤ ሲጸሎትና የእግዚአብሔርን ርዳታ ለመለመን ሌሊትና ቀን ትተጋለች። [6]ምድራዊ ደስታን የምትሻዋ መበለት ግን በሕይወት ብትኖርም የሞተች ናት። [7]ማንም የሚነቀፍበት ነገር እንዳይኖር፣ ይህንም ትእዛዝ ለሕዝቡ ስጥ። [8]አንድ ሰው ዘመዶቹን፣ በተለይም የቅርብ ቤተ ሰቡን የማይረዳ ከሆነ ሃይማኖቱን የካደ፣ ከማያምንም ሰው ይልቅ የባሰ ክፉ ነው። [9]ዕድሜዋ ከሥልሳ ዓመት ያነሰ መበለት በመዝገብ ላይ አትጻፍ፤ ደግሞም የአንድ ባል ሚስት የነበረች[ሰ] ልትሆን ይገባል፤ [10]ልጆችን በማሳደግ፣ እንግዶችን በመቀበል፣ የቅዱሳንን እግር በማጠብ፣ የተቸገሩትን በመርዳትና ለበጎ ምግባር ሁሉ ራሷን በመስጠት በመልካም ሥራም የተመሰከረላት መሆን አለባት።

[11]ወጣት መበለቶችን ግን እንዲህ ባለው መዝገብ አትጻፋቸው፤ ምክንያቱም ሥጋዊ ፍላጎታቸው ለክርስቶስ በገቡት ቃል ላይ በሚያይልበት ጊዜ ለማግባት ይሻሉና። [12]በዚህም ፍርድን በራሳቸው ላይ ያመጣሉ፤ በመጀመሪያ የገቡትን ቃል ኪዳን አፍርሰዋልና። [13]በተጨማሪም ሥራ መፍታትንና ከቤት ቤት መዞርን ይለምዳሉ፤ ሥራ ፈት መሆን ብቻ ሳይሆን፣ የማይገባውን እየተናገሩ ሐሜተኞችና በሰው ጕዳይም ጣልቃ የሚገቡ ይሆናሉ። [14]ስለዚህ ባል የሞተባቸው ወጣት ሴቶች እንዲያገቡ፣ ልጆች እንዲወልዱ፣ ቤታቸውን እንዲያስተዳድሩ፣ ጠላትም የሚነቅፍባቸውን ነገር እንዳያገኝ እመክራለሁ። [15]በእርግጥ ከዚህ በፊት አንዳንዶቹ ሰይጣንን ለመከተል ዘወር ብለዋል።

[16]አማኝ የሆነች ማንኛዋም ሴት በቤተ ሰቧ ውስጥ መበለቶች ቢኖሯት፣ ቤተ ክርስቲያን እውነተኛ መበለቶችን ብቻ መርዳት እንድትችል እርሷው ትርዳቸው እንጂ ለቤተ ክርስቲያን ሸክም እንዲሆኑ አትተዋቸው።

[17]ቤተ ክርስቲያንን በሚገባ የሚያስተዳድሩ፣ ይልቁንም በመስበክና በማስተማር የሚተጉ ሽማግሌዎች ዕጥፍ ክብር ይገባቸዋል፤ [18]መጽሐፍም፣ "እያበራየ ያለውን በሬ አፉን አትሠር፤[*]" ደግሞም፣ "ለሠራተኛ

[ሰ]9 ወይም ለባልዋ ታማኝ የነበረች

[*]18 ዘዳ 25፥4

4፥11 1ጢሞ5፥7፤ 6፥2
4፥12 ፊል3፥17፤ 1ተሰ1፥7፤2ተሰ3፥9፤ 1ጢሞ1፥14፤ 2ጢሞ1፥7፤ ቲቶ2፥7፡15፤1ጴጥ5፥3
4፥13 ሉቃ4፥16፤ ሐሥ13፥14-16፤ ቈላ4፥16፤1ተሰ5፥27፤ 1ጢሞ3፥14
4፥14 ሐሥ6፥6፤ 11፥30፤1ጢሞ1፥18፤ 2ጢሞ1፥6
4፥16 ሮሜ11፥14
5፥1 ዘሌ19፥32፤ ቲቶ2፥2፡6
5፥3 ቍ5፡16
5፥4 ቍ8፤ ሮሜ12፥2፤ ኤፌ5፥10፤6፥1፡2፤1ጢሞ2፥3
5፥5 ቍ3፡16፤ ሉቃ2፥37፤ ሮሜ1፥10፤ 1ቆሮ7፥34፤ 1ጴጥ3፥5
5፥6 ሉቃ15፥24፤
5፥7 1ጢሞ4፥11፤ 6፥2
5፥8 2ጴጥ2፥1፤ ይሁ 4
5፥10 ቍ16፤ ሉቃ7፥44፤ሐሥ9፥36፤ ሮሜ12፥13፤1ጢሞ6፥18፤ 1ጴጥ2፥12
5፥13 ሮሜ1፥29፤ 2ተሰ3፥11
5፥14 1ቆሮ7፥9፤ 1ጢሞ6፥1
5፥15 ማቴ4፥10
5፥16 ቍ3-5
5፥17 ሐሥ11፥30፤ ፊል2፥29፤1ተሰ5፥12
5፥18 ዘሌ19፥13፤ ዘዳ24፥14፡15፤25፥4፤ ማቴ10፥10፤ሉቃ10፥7፤ 1ቆሮ9፥7-9፡14

4፥12 *ወጣትነትህን፤* ጢሞቴዎስ በዚያን ጊዜ ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ወይም ከዚያ ያነሰ ሊሆን ይችላል። በወቅቱ እንዲህ ዐይነቱን ታላቅ የኀላፊነት ቦታ በዚህ ዕድሜ ማግኘት የተለመደ አልነበረም፤ ከዚህም የተነሣ አመራሩ ጥያቄ ውስጥ ሳይገባ አልቀረም።

4፥13 *እኔ እስክመጣ ድረስ፤* ጳውሎስ በዚያን ጊዜ በኤፌሶን በኩል ወደ መቄዶኒያ አልፎ ነበር። ነገር ግን በፍጥነት ወደ ኤፌሶን ተመልሶ ጢሞቴዎስን የማየት ተስፋ እንዳለው ይገልጻል።

4፥14 *በትንቢት፤* የ1፥18 ማብ ይመ።

4፥16 *ራስህንና የሚሰሙህንም ታድናለህ፤* በእርግጥ የሚያድን እግዚአብሔር ብቻ ነው፤ በሌላ በኩል ግን ክርስቲያኖችም ሌሎቹን ወደ ድነት ለማምጣት የእግዚአብሔር መሣሪያ ሊሆኑ ይችላሉ። *ታድናለህ፤* ድነት ድርጊትም ሂደትም ነው። ጌታን እንደ ግል አዳኛችን አድርገን በተቀበልን ጊዜ ድነናል፤ ዳሩ ግን ክርስቶስን ወደ መምሰል ዕለት ዕለት በምናድግበት ጊዜም መዳናችን ይጸናል (1ቆሮ 1፥18)።

5፥3 *በእርግጥ ችግረኛ የሆኑትን መበለቶች ተንከባከባቸው፤* ቍሳዊ ነገሮችን በመስጠት ርዷቸው ማለት ሊሆን ይችላል። በዚያን ዘመን መበለቶች የጡረታ አበል፣ ከመንግሥት የሚሰጥ ርዳታ፣ የሕይወት ዋስትና ወይም እነዚህን የመሳሰሉ ነገሮች ስላልነበሯቸው ለችግር የተጋለጡ ነበሩ።

5፥6 *በሕይወት ብትኖርም የሞተች ናት፤* በሕይወት እያለች በመንፈሳዊ ሕይወቷ የሞተች ናት ማለት ነው።

5፥9 *መዝገብ ላይ፤* የኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን የምትረዳቸውን ባልቴቶች መዝግባ የያዘች ትመስላለች። መበለቶች ከቤተ ክርስቲያን ሽማግሌዎች ደረጃ የሚያስተካክላቸው ማዕረግ መኖሩን የሚያረጋግጥ ማስረጃ ባይኖርም፣ በጸሎት እንዲተጉ (ቍ 5) በጎ ሥራ (ቍ10) እንዲሠሩ ይጠበቅባቸው ነበር።

5፥10 *የቅዱሳንን እግር በማጠብ፤* ሰዎች ሊሠሩት የሚጸየፉት ሥራ ነው፤ ነገር ግን ዐቢይ በመሆኑና የሚያደርጉትም ክፉት ጫማ ስለሆነ ማጠቡ አስፈላጊ ነው (ዮሐ 13፥14 ይመ)።

5፥12 *በመጀመሪያ የገቡትን ቃል ኪዳን አፍርሰዋልና፤* ምናልባት አንዲት መበለት በመዝገብ ውስጥ ስሟ በሚጻፍበት ጊዜ ራሷን ለክርስቶስ ታስገዛ ነበር፤ ነገር ግን ዳግም ስታገባ ይህ ትጋት ቀንሶ ሊሆን ይችላል፤ ወይም ጳውሎስ አንዲት መበለት ከእምነቷ ውጭ የሆነ ጋብቻ ለመፈጸም የምታደርገውን ማወላወል ክርስቲያኖች በክርስቶስ ካላቸው እውነተኛ መታመን ጋር ሊያነጻጽር ፈልጎ ሊሆን ይችላል።

5፥15 *ሰይጣን* የዘፍ 3፥1፤ ማቴ 16፥23፤ ቈላ 3፥5 ማብ ይመ።

*5፥17፤* ሽማግሌዎች ሁሉ፣ መሪዎች ናቸው ( 3÷ 4 –5) ፤ ይኸውም፣ ማስተማርና መስበክ ነው (3÷2)፤ እነዚህም ሊከበሩ ይገባቸዋል። ይለቁንም በመሪነታቸው በተለይም በማስተማርና በመስበክ የሚደክሙት ግን ዕጥፍ ክብር ማግኘት ይገባቸዋል፤ እንዲህ ዐይነቱ ክብር የገንዘብንም ድጋፍ እንደሚያጠቃልል በቍጥር 18 ላይ የቀረቡት ሁለቱ መግለጫዎች ይጠቍማሉ።

5፥18 *መጽሐፍ፤* ቃሉ የብሉይንና (ዘዳ 25፥4) እና አዲስን

ደመወዙ ይገባዋል[ሀ]" ይላልና። [19]በሁለት ወይም በሦስት ምስክሮች ካልተደገፈ በቀር በሽማግሌ ላይ የሚቀርብ ክስ አትቀበል። [20]ሌሎች አይተው እንዲጠነቀቁ ኀጢአት የሚሠሩትን በጉባኤ ፊት ገሥጻቸው።

[21]በእግዚአብሔርና በክርስቶስ ኢየሱስ፣ በተመረጡትም መላእክት ፊት እነዚህን ትእዛዛት ያለ አድልዎ እንድትጠብቅና አንዳችም ነገር በማበላለጥ እንዳታደርግ ዐደራ እልሃለሁ።

[22]በማንም ላይ እጅ ለመጫን አትቸኰል፤ ከሌሎችም ጋር በኀጢአት አትተባበር፤ ራስህን በንጽሕና ጠብቅ።

[23]ለሆድህና ደጋግሞ ለሚነሣብህ ሕመም፣ ጥቂት የወይን ጠጅ ጠጣበት እንጂ ከእንግዲህ ውሃ ብቻ አትጠጣ።

[24]የአንዳንድ ሰዎች ኀጢአት ግልጽ ነው፤ ከእነርሱም ቀድሞ ፍርድ ቦታ ይደርሳል፤ ሌሎችን ግን ኀጢአታቸው ይከተላቸዋል። [25]መልካም ሥራም እንደዚሁ ግልጽ ነው፤ ግልጽ ያልሆነ ቢኖርም እንኳ ተሰውሮ አይቀርም።

6 የእግዚአብሔር ስምና ትምህርቱም እንዳይሰደቡ፣ በባርነት ቀንበር ሥር ያሉ ሁሉ፣ ጌቶቻቸው ሙሉ ክብር እንደሚገባቸው አድርገው ይቍጠሩ። [2]የሚያምኑ ጌቶች ያሏቸውም፣ ወንድሞች ስለ ሆኑ የሚገባቸውን ክብር አይንፈጓቸው፤ ይልቁንም በአገልግሎታቸው የሚጠቀሙ አማኞችና ወዳጆቻቸው ስለሆኑ የበለጠ ሊያገለግሏቸው ይገባል። እነዚህን ነገሮች አስተምር፤ ምከርም።

### የገንዘብ ፍቅር

[3]ማንም የሐሰት ትምህርት ቢያስተምር፣ ከጌታችን ከኢየሱስ ክርስቶስ ጤናማ ቃልና እውነተኛ መንፈሳዊነትን ከሚያጐለብት ትምህርት ጋር የማይስማማ ቢሆን፣ [4]ያ ሰው በትዕቢት ተወጥሮአል፤ አንዳችም አያስተውልም። ስለ ቃላት ለመከራከርና ለመጣላት ክፉ ጕጕት አለው፤ እነዚህም ቅናትን፣ ጥልን፣ ስድብን፣ መጥፎ ጥርጣሬን ያስከትላሉ፤ [5]እውነትን በተቀሙና መንፈሳዊው ነገር ትርፍ ማግኛ በሚመስላቸውና አእምሮ በጐደላቸው ሰዎች መካከል የማያባራ ንትርክ ያመጣሉ።

[6]ነገር ግን እውነተኛ መንፈሳዊነት ባለን ነገር ከመርካት ጋር ትልቅ ትርፍ ነው። [7]ምክንያቱም ወደ ዓለም ያመጣነው ምንም ነገር የለም፤ ምንም ነገር ይዘን መሄድም አንችልም። [8]ነገር ግን ምግብና ልብስ ካለን፣ ያ ይበቃናል። [9]ባለጠጋ ለመሆን የሚፈልጉ ግን ወደ ፈተናና ወደ ወጥመድ፣ እንዲሁም ሰዎችን ወደ መፍረስና ወደ ጥፋት ወደሚያዘቅጠው ወደ ብዙ ከንቱና ክፉ ምኞት ይወድቃሉ። [10]ምክንያቱም የገንዘብ ፍቅር የክፋት ሁሉ ሥር ነው፤ አንዳንዶች ባለጠጋ ለመሆን ካላቸው ጕጕት የተነሣ ከእምነት መንገድ ስተው ሄደዋል፤ ራሳቸውንም በብዙ ሥቃይ ወግተዋል።

### ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ የሰጠው ዐደራ

[11]የእግዚአብሔር ሰው ሆይ፤ አንተ ግን ከዚህ ሁሉ ሽሽ፤ ጽድቅን፣ እውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወትን፣ እምነትን፣ ፍቅርን፣ ትዕግሥትንና ገርነትን ተከታተል። [12]መልካሙን የእምነት ገድል ተጋደል፤ በብዙ ምስክሮች ፊት በመልካም መታመን የመሰከርህለትንና የተጠራህበትን የዘላለም ሕይወት አጥብቀህ ያዝ። [13]ለሁሉም ሕይወትን በሚሰጥ በእግዚአብሔር ዘንድ እንዲሁም በጳንጥዮስ ጲላጦስ ፊት እውነትን በመሰከረ በክርስቶስ ኢየሱስ ፊት ዐደራ የምልህ፣ [14]ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እስኪገለጥ ድረስ፣ ይህን ትእዛዝ ያለ ዕድፍና ያለ ነቀፋ ሆነህ እንድትጠብቅ ነው፤ [15]ያም መገለጥ፣ የተባረከውና ብቻውን ገዥ የሆነው

ሀ18 ሉቃ 10፥7

5፥19 ማቴ18፥16፤ ሐሥ11፥30
5፥20 ዘዳ13፥11፤ 2ጢሞ4፥2፤ ቲቶ1፥13፤2፥15
5፥21 1ጢሞ6፥13፤ 2ጢሞ4፥1
5፥22 መዝ18፥26፤ ሐሥ6፥6፤ኤፌ5፥11
5፥23 1ጢሞ3፥8
6፥1 ኤፌ6፥5፤ 1ጢሞ5፥14፤ ቲቶ2፥5፡8
6፥2 1ጢሞ4፥11፤ ፊሞ16
6፥3 1ጢሞ1፥3፡10
6፥4 1ጢሞ3፥6፤ 2ጢሞ2፥14፤3፥4
6፥5 2ጢሞ3፥8፤ ቲቶ1፥15
6፥6 ፊል4፥11፤ 1ጢሞ4፥8፤ዕብ13፥5
6፥7 ኢዮ1፥21፤ መዝ49፥17፤መክ5፥15
6፥8 ምሳ30፥8፤ ዕብ13፥5
6፥9 ምሳ15፥27፤ 28፥20፤1ጢሞ3፥7
6፥10 ቍ21፤ ኢሱ7፥21፤ 1ጢሞ3፥3፤5፥19
6፥11 ቍ3፡5፡6፤ 1ጢሞ1፥14፤2፥2፤ 2ጢሞ2፥22፤3፥10፤ 3፥17
6፥12 ቍ19፤ ማቴ25፥46፤1ቆሮ9፥25፡ 26፤ፊል3፥12፤ 1ጢሞ1፥18፤ዕብ3፥1
6፥13 ቍ12፤ ዮሐ18፥33-37፤ 1ጢሞ5፥21፤ 2ጢሞ4፥1
6፥14 1ቆሮ1፥7፤ 1ተሰ3፥13፤ 2ጢሞ1፥10፤4፥1፡8
6፥15 ዘዳ10፥17፤ መዝ136፥3፤ዳን2፥47፤ 1ጢሞ1፥11፡17፤ 2፥6፤ቲቶ1፥3፤ራእ1፥5፤ 17፥14፤19፥16

ኪዳን (ሉቃ 10፥7) መጻሕፍትን የሚያሳይ ነው፤ ይህም የሚያሳየን በዚያን ወቅት የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት (ጥቂት መጻሕፍት) ከብሉይ ኪዳን መጻሕፍት እኩል ሥልጣን እንዳላቸው መታየት እንደ ጀመሩ ነው።

5፥20 *ኀጢአት የሚሠሩትን፤* ጳውሎስ፣ ሽማግሌዎች ላይም የሥነ ሥርዐት ርምጃ ሊወሰድባቸው እንደሚገባ ያመለክታል።

5፥21 *በተመረጡትም መላእክት፤* ከሰይጣንና ከሌሎቹ ከወደቁ መላእክት ጋር የሚነጻጸር ነው።

5፥22 *በማንም ላይ እጅ ለመጫን አትቸኩል፤* ጳውሎስ እያለ ያለው፣ ለዚህ ቦታ የታጨ ሰው ኀላፊነቱን በሚገባ ለመወጣት ብቃት ያለው መሆኑን ለማሳየት እንዲችል በቂ ጊዜ ሳይሰጠውና ይህም ሳያረጋግጥ፣ አንዱን ሰው የቤተ ክርስቲያን እረኛ አድርጎ መሾም ተገቢ እንዳልሆነ ነው። *ከሌሎችም ጋር በኀጢአት አትተባበር፤* ለሽምግልና አገልግሎት ተገቢ ያልሆነውን ሰው አትሹም። *ራስህን በንጽሕና ጠብቅ፤* ተገቢ ያልሆነውን ሰው በመሾም ተሳትፎ አለማድረግን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል።

5፥23 *ውሃ ብቻ አትጠጣ፤* ጳውሎስ ስለ ቤተ ክርስቲያን እረኞች በጻፈው መልእክቱ ውስጥ ተጨማሪ ሆኖ የገባ ምክር ነው፤ ጢሞቴዎስ ለነበረ ሥጋዊ ሕመም፣ ምናልባት ንጹሕ የመጠጥ ውሃ ማግኘት አስቸጋሪ በሚሆንበት ጊዜ ጥቂት የወይን ጠጅ እንዲጠጣ ጳውሎስ ምክር ይለግሠዋል።

5፥24-25 *የአንዳንድ ሰዎች ኀጢአት…መልካም ሥራም ፤* መልካም መልካሙን ሥራ ማየት ብቻ ሳይሆን፣ በተሸሸገው ዕጩ ሕይወት ውስጥ የተደበቁ ኀጢአቶችም ሊኖሩ ስለሚችሉ እነዚህን ለማወቅ ንቁ ሆኖ መገኘት እንደሚያስፈልግ ጳውሎስ ይመክራል።

6፥1 *በባርነት፤* የኤፌ 6፥5፤ የቈላ 3፥22-4፥1 ማብ ይመ።

6፥2 *አስተምር፤ ምከርም፤* ለባሮች የተሰጠውን መመሪያ ያመለክታል።

*6፥3-5፤* ጳውሎስ በ1፥3 ላይ ወዳለው ትምህርት ይመለሳል። የ1፥3-11 ማብ ይመ።

6፥5 *እውነትን በተቀሙ፤* በአንድ ወቅት እውነትን ያወቁ፣ በኋላ ግን ወደ ስሕተት ጐዳና ያመሩ ናቸው። *መንፈሳዊ ነገር ትርፍ ማግኛ በሚመስላቸው፤* የ2ቆሮ 11፥7 ማብ ይመ።

6፥11 *እውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወትን፤* የ2፥2 ማብ ይመ።

6፥12 *በመልካም መታመን የመሰከርህለትን፤* ጢሞቴዎስ በመጀመሪያው የጳውሎስ የወንጌል ጕዞ ወቅት በተጠመቀ ጊዜ እምነቱ የተገለጸበትን የሚያሳይ ነው። *የዘላለም ሕይወት አጥብቀህ ያዝ፤* ጢሞቴዎስ ቀደም ብሎ የዳነ ስለ ሆነ የዘላለም ሕይወት አለው፤ ነገር ግን ጳውሎስ ጠቀሜታውን በሙላት እንዲያውጅ ያበረታታዋል (ቍ17-19 እና የ4፥16 ማብ ይመ)።

6፥13 *በጳንጥዮስ በጲላጦስ ፊት እውነትን በመሰከረ፤* በዮሐ 18፥33-37፤ 19፥10-11 የተጠቀሰውን የኢየሱስን ንግግር ሳያመለክት አይቀርም።

6፥14 *ይህን ትእዛዝ፤* ወንጌልን እንዲሰብክና ቤተ ክርስቲያንን እንዲንከባከብ ለጢሞቴዎስ የተሰጠውን ኀላፊነት ያመለክታል (ቍ 20)።

የነገሥታት ንጉሥ፣ የጌቶችም ጌታ እግዚ
አብሔር በራሱ ጊዜ የሚያሳየው ነው፤ [16]እርሱ
ብቻ ኢመዋቲ ነው፤ ሊቀረብ በማይቻል
ብርሃን ውስጥ ይኖራል፤ እርሱን ያየ ማንም
የለም፤ ሊያየውም የሚችል የለም። ለእርሱ
ክብርና ኀይል ከዘላለም እስከ ዘላለም
ይሁን፤ አሜን።

[17]በዚህ ዓለም ባለጠጎች የሆኑት እንዳይ
ታበዩ፣ ደስም እንዲለን ሁሉን ነገር አትረ
ፍርፎ በሚሰጠን በእግዚአብሔር እንጂ አስተ
ማማኝነት በሌለው በሀብት ላይ ተስፋ እን
ዳያደርጉ እዘዛቸው። [18]መልካም እንዲሠሩ፣
ቸሮችና ለማካፈል ፈቃደኞች የሆኑ እንዲ
ሆኑ እዘዛቸው። [19]በዚህ ዐይነት እውነተኛ
የሆነውን ሕይወት ያገኙ ዘንድ፣ ለሚመ
ጣው ዘመን ጽኑ መሠረት የሚሆን ሀብት
ለራሳቸው ያከማቻሉ።

[20]ጢሞቴዎስ ሆይ፤ በዐደራ የተቀበልኸ
ውን ሁሉ ጠብቅ፤ እግዚአብሔርን ከማያስ
ከብር ከከንቱ ልፍለፋና በውሸት ዕውቀት
ከተባለ የተቃውሞ ፍልስፍና ራቅ፤ [21]የዚህ ዐይ
ነት ዕውቀት አለን ሲሉ የነበሩ አንዳን
ዶች ይህን በማድረጋቸው ከእምነት መን
ገድ ስተው ሄደዋል።

ጸጋ ከእናንተ ጋር ይሁን።

6፥16 መዝ104፥2፤ ዮሐ1፥18፤ ሮሜ11፥36፤ 1ጢሞ1፥17፤ 1ዮሐ1፥7
6፥17 ቀ-9፤ መዝ62፥10፤ ኤር49፥4፤ሉቃ12፥20፡21፤ሐሥ14፥17፤ 1ጢሞ4፥10
6፥18 ሮሜ 12፥8፡13፤ኤፌ4፥28፤ 1ጢሞ5፥10
6፥19 ቀ-12፤ ማቴ6፥20፤ኤፌ3፥12

6፥20 2ጢሞ1፥12፡ 14፤2፥16 6፥21 ቀ-10፤ ቈላ4፥18፤2ጢሞ2፥18

6፥15 *የነገሥታት ንጉሥ፣ የጌቶችም ጌታ፤* ራእ 19፥16 ይመ። *በራሱ ጊዜ፤* የኢየሱስ የመጀመሪያ ምጽአት እግዚአብሔር በፈቀደበት በትክክለኛው ጊዜ እንደሆነ ሁሉ (ገላ 4፥4)፣ ዳግም ም ጽአቱም እንደዚሁ ይሆናል።

6፥16 *እርሱን ያየ ማንም የለም፤ ሊያየውም የሚችል የለም፤* ዮሐ 1፥18 ይመ።

6፥19 *ሕይወት ያገኙ ዘንድ፤* የቀ- 12 ማብ ይመ።

6፥20 *በዐደራ የተቀበልኸውን፤* ወንጌልን ማለቱ ነው። በ2ጢሞ 1፥14 ላይም ተመሳሳይ ትእዛዝ ይገኛል። *በውሸት ዕው ቀት ከተባለ፤* አንድ ሰው ዕውቀት ካለው ይድናል ብሎ የሚያስተምረውን የመጀመሪያውን የኖስትሳውያን ትምህርት የሚያመለክት ነው። ኖስትስ የሚለው ቃል ዕውቀት ከሚለው የግሪክ ቃል የመጣ ነው። (ከ1ዮሐንስ መግቢያ፣ "ኖስትሳውያን ትምህርት" የሚለውን ይመ)።

6፥21 *ጸጋ ከአንተ ጋር ይሁን፤* በግሪኩ፣ "እንተ" የሚለው ቃል የብዙ ቍጥር ማመልከቱ፣ ጳውሎስ መልእክቱን የጻፈው ለጢሞቴዎስ ቢሆንም እንኳ ለመላው የኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን ማኅበረ ምእመናን እንዲነበብ መፈለጉን ያመለክታል።

# የሐዋርያው ጳውሎስ መልእክት
# ወደ ጢሞቴዎስ - ሁለተኛ

## መግቢያ

**በገጽ** 1835 **ላይ "መልእክታተ ምጋቤ" የሚለውን ይመ።**

**ጸሐፊው፣ መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ**

ጳውሎስ በ62/63 ዓ.ም. ከሮም እስር ቤት ከተለቀቀ በኋላና (ሐሥ 28) የመጀመሪያውን የጢሞቴዎስን መልእክትና የቲቶን መልእክት ከጻፈበት ከአራተኛው ሐዋርያዊ የወንጌል ጉዞው በኋላ በንጉሠ ነገሥት ኔሮ ዘመነ መንግሥት በ66-67 ዓ.ም. በድጋሚ ታስሮ ነበር። 2ኛ ጢሞቴዎስንም የጻፈው በዚህ ጊዜ ነበር። ጳውሎስ በመጀመሪያው እስራቱ ወቅት ቤት ተከራይቶ ይኖር ነበር (ሐሥ 28፥30)፤ በሁለተኛው ግን ከምድር በታች ባለ ቀዝቃዛ እስር ቤት ውስጥ (4፥13) እንደ ማንኛውም ወንጀለኛ በሰንሰለት ታስሮ ተንገላቷል (1፥16፤ 2፥9)። ጓደኞቹ የት እንደ ታሰረ እንኳ ለማወቅ ከፍተኛ ችግር ገጥሞአቸው ነበር (1፥17)። ሐዋርያው በእርሱ አማካይነት መሠራት የሚገባው ሥራ እንደተጠናቀቀ እና የሕይወቱ ፍጻሜ እንደቀረበ ዐውቆአል (4፥6-8)።

**የተጻፈበት ዐላማ**

**ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ ይህን መልእክት እንዲጽፍ ያደረጉት ሦስት ምክንያቶች ነበሩት:-**

1) ጳውሎስ ብቸኛ ሆኖ ነበረ፤ ፊሎጎስና ሔርሞጌኔስ፣ በእስያ አውራጃ ያሉት የሥራ ጓደኞቹ ሁሉ (1፥15)፣ ዴማስም (4፥10) ትተውት ሄደዋል። ቄርቂስ፣ ቲቶና ቲኪቆስም በአጠገቡ አልነበሩም (4፥10-12)፤ ከእርሱ ጋር የነበረው ሉቃስ ብቻ ነው (4፥11)። ጢሞቴዎስ ልጅ አባቱን እንደሚያገለግል ከጳውሎስ ጋር ሆኖ ያገለገለ (ፊል 2፥22፤ 1ቆሮ 4፥17 ይመ) የጳውሎስ የሥራ ባልደረባ (ሮሜ 16፥21) ነበር። ጳውሎስም "ስለ እናንተ ደኅንነት ከልብ የሚገደው እንደ እርሱ ማንም የለኝም" በማለት መስክሮለታል (ፊል 2፥20)። ጳውሎስ ጢሞቴዎስን ከመናፈቁ የተነሣ በአስቸኳይ ወደ እርሱ እንዲመጣ (1፥4) ሁለት ጊዜ ጠይቈታል (4፥9፡21)። ስለ ጢሞቴዎስ በበለጠ ለማወቅ ከ1ኛ ጢሞቴዎስ መግቢያ "የመልእክቱ ተደራሲ" የሚለውን ይመ።

2) ጳውሎስ በኔሮ ዘመን ከነበረው ስደት የተነሣ ስለ ቤተ ክርስቲያን በጣም ይጨነቅ ነበር፤ ጢሞቴዎስንም የወንጌል ዐደራ እንዲጠብቅ (1፥4)፣ በእርሱም እንዲጸና (3፥14)፣ የስብከት አገልግሎቱን እንዳያቋርጥና (4፥2) አስፈላጊም ከሆነ ስለ ወንጌል መከራን እንዲቀበል ይመክረዋል (1፥8፤ 2፥3)።

3) በጢሞቴዎስ በኩልም ለኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን መጻፍ ፈልጎአል (የ4፥22 ማብ ይመ)

**አስተዋፅኦ**

1. መግቢያ (1፥1-4)
2. ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ መጨነቁ (1፥5-14)
3. ጳውሎስ የነበረበት ሁኔታ (1፥15-18)
4. ለጢሞቴዎስ የተሰጠ ልዩ መመሪያ (ም 2)
   - ሀ. ለትዕግሥት የቀረበ ጥሪ (2፥1-13)
   - ለ. ከአጉል ክርክር እንዲርቅ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ (2፥14-26)
5. ስለ መጨረሻው ዘመን የተሰጠ ማስጠንቂያ (ም 3)
   - ሀ. የሚያስጨንቁ ዘመናት (3፥1-9)
   - ለ. ዘመናቱን የመዋጊያ ዘዴዎች (3፥10-17)
6. የጳውሎስ የስንብት ንግግር (4፥1-7)
   - ሀ. ቃሉን እንዲሰበክ የሰጠው ትእዛዝ (4፥1-5)
   - ለ. የጳውሎስ የድል ተስፋ (4፥6-8)
7. የመጨረሻ ሰላምታ (4፥9-22)

1 በክርስቶስ ኢየሱስ ቃል በተገባው የሕይወት ተስፋ መሠረት፣ በእግዚአብሔር ፈቃድ የክርስቶስ ኢየሱስ ሐዋርያ የሆነ ጳውሎስ፤

[2]ለተወዳጁ ልጄ፣ ለጢሞቴዎስ፤

ጸጋ፣ ምሕረትና ሰላም ከእግዚአብሔር አብ፣ ከጌታችንም ከክርስቶስ ኢየሱስ ይሁን።

*ታማኝ ስለ መሆን የተሰጠ ማበረታቻ*

[3]ሳላቋርጥ ሌሊትና ቀን በጸሎቴ ስለ አንተ ሳስብ፣ ቀደምት አባቶች እንዳደረጉት በንጹሕ ኅሊና የማመልከውን እግዚአብሔርን አመሰግናለሁ። [4]ዕንባህን እያስታወስሁ በደስታ እሞላ ዘንድ ላይህ እናፍቃለሁ። [5]ግብዝነት የሌለበት እምነትህን አስታውሳለሁ፤ ይህ እምነት ቀድሞ በአያትህ በሎይድ እንዲሁም በእናትህ በኤውንቄ ዘንድ ነበረ፤ አሁን ደግሞ በአንተ እንዳለ ተረድቻለሁ። [6]ስለዚህ በእጆቼ መጫን የተቀበልኸውን በአንተ ውስጥ ያለውን የእግዚአብሔርን ስጦታ እንድ ታቀጣጥል አሳስብሃለሁ፤ [7]እግዚአብሔር የኀይልና የፍቅር፣ ራስንም የመግዛት መንፈስ እንጂ የፍርሀት መንፈስ አልሰጠንምና።

[8]እንግዲህ፣ ስለ ጌታችን ለመመስከር ወይም የእርሱ እስረኛ በሆንሁት በእኔ አትፈር፤ ነገር ግን በእግዚአብሔር ኀይል ስለ ወንጌል ከእኔ ጋር መከራን ተቀበል፤ [9]እኛ ስላደረግነው አንዳች ነገር ሳይሆን ከዕቅዱና ከጸጋው የተነሣ ያዳነን ወደ ቅዱስ ሕይወትም የጠራን እርሱ ነው። ይህም ጸጋ ከዘላለም ዘመናት በፊት በክርስቶስ ኢየሱስ ተሰጠን፤ [10]አሁን ግን ሞትን ደምስሶ በወንጌል አማካይነት ሕይወትንና ኢመዋቲነትን ወደ ብርሃን ባወጣው በመድኀኒታችን፣ በክርስቶስ ኢየሱስ መምጣት ተገልጦአል። [11]እኔም ለዚህ ወንጌል የምሥራች ነጋሪና ሐዋርያ፣ አስተማሪም ሆኜ ተሾምሁ። [12]መከራን የምቀበለውም ለዚሁ ነው፤ ሆኖም ያመንሁትን እርሱን ስለ ማውቅ አላፍርበትም፤ የሰጠሁትንም ዐደራ እስከዚያች ቀን ድረስ መጠበቅ እንደሚችል ተረድቻለሁ።

[13]ከእኔ የሰማኸውን በክርስቶስ ኢየሱስ ባለ እምነትና ፍቅር፣ የጤናማ ትምህርት ምሳሌ አድርገህ ያዝ። [14]የተሰጠህን መልካሙን ዐደራ፣ በእኛ ውስጥ በሚኖረው በመንፈስ ቅዱስ ጠብቅ።

[15]በእስያ አውራጃ ያሉት ሁሉ እንደ ተዉኝ ታውቃለህ፤ ከእነርሱም መካከል ፊሎጎስና ሄርሞጌኔስ ይገኛሉ።

[16]ጌታ ለሄኔሲፎሩ ቤተ ሰዎች ምሕረትን ይስጥ፤ ምክንያቱም ብዙ ጊዜ ቸርነት አድርጎልኛል፤ በታሰርሁበትም ሰንሰለት አላፈረም። [17]እንዲያውም ወደ ሮም በመጣ ጊዜ ፈልጎ ፈልጎ አገኘኝ። [18]በዚያች ቀን ምሕረትን ከጌታ ያገኝ ዘንድ ጌታ ይስጠው፤ በኤፌሶንም የቱን ያህል እንዳገለገለኝ አንተ በሚገባ ታውቃለህ።

2 እንግዲህ ልጄ ሆይ፤ አንተ በክርስቶስ ኢየሱስ ባለው ጸጋ በርታ። [2]በብዙ ምስክር ፊት ከእኔ የሰማኸውን፣ ሌሎችን ለማስተማር ብቃት ላላቸው ለታመኑ ሰዎች ዐደራ ስጥ። [3]እንደ ክርስቶስ ኢየሱስ በጎ

1፥1 1ቆሮ1፥1፤ 2ቆሮ1፥1፤ኤፌ3፥6፤ 1ጢሞ6፥19፤ቲቶ1፥2
1፥2 ሐሥ16፥1፤ ሮሜ1፥7፤1ጢሞ1፥2
1፥3 ሐሥ23፥1፤ ሮሜ1፥8፡10
1፥4 ሐሥ20፥37፤ 2ጢሞ4፥9
1፥5 ሐሥ16፥1፤ 1ጢሞ1፥5፤2ጢሞ3፥15
1፥6 ሐሥ6፥6፤1ጢሞ4፥14
1፥7 ኢሳ11፥2፤ ኤር42፥11፤ ሮሜ8፥15፤ 1ቆሮ16፥10፡11፤ 1ጢሞ4፥12፤ዕብ2፥15
1፥8 ቁ-12፡16፤ ማር8፥38፤ኤፌ3፥11፤ 2ጢሞ2፥3፡9፤4፥5
1፥9 ሮሜ8፥28፤ 11፥14፤ኤፌ2፥9
1፥10 1ቆሮ15፥26፡ 54፤ኤፌ1፥9፤ 1ጢሞ6፥14
1፥11 ቁ-8፤ሐሥ9፥15፤ 1ጢሞ2፥7
1፥12 ቁ-8፡14፡16፡ 18፤ማር8፥38፤ 1ቆሮ8፥38፤1ቆሮ1፥8፤ 1ጢሞ6፥20፤ 2ጢሞ4፥8
1፥13 ሮሜ6፥17፤ 1ተሰ1፥3፤ 1ጢሞ1፥10፡14፤ 2ጢሞ2፥2፤ቲቶ1፥9
1፥14 ቁ-12፤ሮሜ8፥9
1፥15 ሐሥ2፥9፤ 2ጢሞ4፥19
1፥18 ቁ-12፤ ሐሥ18፥19፤ዕብ6፥10

2፥1 ኤፌ6፥10፤ 1ጢሞ1፥2 2፥2 1ጢሞ6፥12፤2ጢሞ1፥13
2፥3 ቁ-9፤1ጢሞ1፥18፤ 2ጢሞ1፥8፤4፥5

1፥1 *በክርስቶስ ኢየሱስ በሚገኘው የሕይወት ተስፋ፤* ሐዋርያት የተሾሙት ለሚቀበሉ ሁሉ የዘላለም ሕይወትን በነፃ የሚሰጥ መሆኑን ለማስተማርና ለመስበክ በመሆኑ፣ ጳውሎስም ሐዋርያ ሆኖ የተመረጠው ይህን ተስፋ እዳር ለማድረስ ነው። *ሐዋርያ፤* ልዩ በሆነ ሁኔታ ከራሱ ከክርስቶስ አገልግሎት የተቀበለ ማለት ነው (የማር 6፥30፤ 1ቆሮ 1፥1፤ ዕብ 3፥1 ማብ ይመ)።

1፥2 *ለተወዳጁ ልጄ፣ ለጢሞቴዎስ፤* የ1ጢሞ 1፥2 ማብ ይመ። *ጸጋ...ሰላም፤* የዮና 4፥2፤ ዮሐ 14፥27፤ 20፥19፤ ገላ 1፥3፤ የኤፌ 1፥2 ማብ ይመ።

1፥3 *በጸሎቴ...እግዚአብሔርን አመሰግናለሁ፤* የፊል 1፥3-4 ማብ ይመ።

1፥4 *እንባህን እያስታወስሁ፤* ጳውሎስ ወደ መቄዶኒያ ለመሄድ በተነሣ ጊዜ ጢሞቴዎስ ሲሸኘው እንባውን ሳያፈስ እንዳልቀረ ያሳያል (1ጢሞ 1፥3)። *ላይህ እናፍቃለሁ፤* 4፥9፡21 ይመ።

1፥5 *በአያትህ በሎይድ...በእናትህ በኤውንቄ፤* በሐሥ 16፥1 ላይ ተጽፎ እንደምናነበው የጢሞቴዎስ እናት አይሁዳዊ ክርስቲያን ነበረች፤ በዚህ ስፍራ ደግሞ አያቱ ክርስቲያን እንደ ነበረች ተገልጾአል። አባቱ ግን ግሪካዊ ነው፤ እንዲሁም አማኝ አልነበረም (ሐሥ 16፥1)። ምናልባት ያልተገረዘው በዚህ ምክንያት ነው።

1፥6 *በእጆቼ መጫን፤* ጳውሎስ፣ የመንፈስ ቅዱስ ስጦታ በእርሱ አማካይነት ለጢሞቴዎስ የተላለፈበት የእግዚአብሔር መሣሪያ ነበር (የ1ጢሞ 1፥18 ማብ ይመ)። *የእግዚአብሔርን ስጦታ እንድታቀጣጥል፤* መንፈሳዊ ስጦታዎች በአጠቃቀም ሂደት የሚያድጉ እንጂ እንዲሁ አድገው የሚሰጡ አይደሉም።

1፥7 *እግዚአብሔር... የፍርሀት መንፈስ አልሰጠንምና፤* የጢሞቴዎስ ትልቁ ችግር ድፍረት ማጣቱ ነበር (1ቆሮ 16፥10-11፤ 1ጢሞ 4፥12 ይመ)።

1፥9 *ከዕቅዱና ከጸጋው የተነሣ ያዳነን ወደ ቅዱስ ሕይወትም የጠራን እርሱ ነው፤* ድነት በእግዚአብሔር ዕቅድና በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ ነጻ ስጦታ የሚገኝ እንጂ በሰው ጥረት ላይ የተመሠረተ አይደለም (ሮሜ 3፥28፤ ኤፌ 2፥8-9፤ ቲቶ 3፥5 ይመ)። *ከዘላለም ዘመናት በፊት፤* እግዚአብሔር የጠፉትን ለማዳን ያቀደው ከዘላለም በፊት ነው (ኤፌ 1፥4፤1ጴጥ 1፥20፤ ራእ 13፥8 ይመ)

1፥11 *የምሥራች ነጋሪና ሐዋርያ፤* የ1ጢሞ 2፥7 ማብ ይመ።

1፥12 *እስከዚያች ቀን፤* የፍርድ ቀን ለማለት ነው።

1፥13 *በክርስቶስ ኢየሱስ ባለ እምነትና ፍቅር፤* ከክርስቶስ ጋር ኅብረት በማድረግ የሚገኝ እምነትና ፍቅር ማለት፣ "የክርስቲያናዊ እምነትና ፍቅር" ማለት ነው (1ጢሞ 1፥14 ይመ)። *የጤናማ ትምህርት፤* የቲቶ 1፥9 ማብ ይመ።

1፥14 *የተሰጠህን መልካሙን ዐደራ፤* ወንጌልን ነው። ጳውሎስ በ1ጢም 6፥20 ላይም ተመሳሳይ ትእዛዝ ይሰጣል።

1፥15 *በእስያ አውራጃ፤* ጢሞቴዎስ በዛሬዪቱ የቱርክ ግዛት በምዕራቡ ክፍል በምትገኘው የቀድሞዋ የእስያ አውራጃ ከተማ በሆነችው በኤፌሶን ይገኝ ነበር። *ሁሉ፤* ብዙ ሰው እንደተወው ለማመልከት የገባ ነው። *ፊሎጎስና ሄርሞጌኔስ፤* ስለ እነዚህ ሁለት ሰዎች የሚታወቅ ነገር የለም።

1፥16 *ሄኔሲፎሩ፤* እርሱና ቤተ ሰቡ የኤፌሶን ነዋሪዎች ሳይሆኑ አይቀሩም (ቁ 18፤ 4፥19)።

1፥17 *ሮም፤* መግቢያውን ይመ፤ እንዲሁም ቁ-8፤ 2፥9 ይመ።

1፥18 *በዚያች ቀን፤* በፍርድ ቀን ማለት ነው። *በኤፌሶንም የቱን ያህል እንዳገለገለኝ፤* በሦስተኛው ወይም በአራተኛው የጳውሎስ የወንጌል ጉዞ ወቅት ማለት ነው (አራተኛው የጳውሎስ ጉዞ የሚለውን ከ□ ይመ)።

2፥1 *ልጄ፤* የ1ጢሞ 1፥2 ማብ ይመ ።

2፥2 *በብዙ ምስክር ፊት፤* በሦስቱም የጳውሎስ የወንጌል ጉዞዎች ጢሞቴዎስ ደጋግሞ የሰማውን የጳውሎስን ስብከቶችና ትምህርቶች ያመለክታል።

*2፥3-6፤* ጢሞቴዎስ እንዲከተላቸው ጳውሎስ የሰጠው ሦስት ምሳሌዎች፦ 1)አለቃውን ለማስደሰት የሚፈልግ ወታደር

ወታደር፣ ከእኛ ጋር መከራን ተቀበል:: 4በውትድርና የሚያገለግል ሰው አዛዡን ለማስደሰት ይጥራል እንጂ በሌላ ሥራ ራሱን አያጠላልፍም:: 5እንደዚሁም በውድድር የሚሳተፍ ሰው፣ የውድድሩን ሕግ ጠብቆ ካልተወዳደረ የድሉን አክሊል አያገኝም:: 6ትጉሕ ገበሬም ከሰብሉ ለመጠቀም የመጀመሪያው ሊሆን ይገባዋል:: 7እኔ የምለውን ልብ በል፤ ጌታ በሁሉም ነገር ማስተዋልን ይሰጥሃልና::

8ከሙታን የተነሣውን፣ ከዳዊት ዘርም የሆነውን ኢየሱስ ክርስቶስን አስብ፤ የእኔም ወንጌል ይኸው ነው፤ 9ለዚህም እንደ ወንጀለኛ እስከ መታሰር ድረስ መከራን እየተቀበልሁ ነው፤ የእግዚአብሔር ቃል ግን አይታሰርም:: 10ስለዚህ በክርስቶስ ኢየሱስ ያለውን መዳን ከዘላለም ክብር ጋር እነርሱም ያገኙ ዘንድ፣ ለተመረጡት ስል ሁሉንም በመታገሥ እጸናለሁ::

11እንዲህ የሚለው ቃል የታመነ ነው፤
ከእርሱ ጋር ከሞትን፣
ከእርሱ ጋር ደግሞ በሕይወት እንኖራለን፡፡
12ብንጸና፣
ከእርሱ ጋር ደግሞ እንነግሣለን::
ብንክደው፣
እርሱ ደግሞ ይክደናል፤
13ታማኞች ሆነን ባንገኝ
እርሱ ታማኝ እንደ ሆነ ይኖራል፤
ራሱን መካድ አይችልምና::

## እግዚአብሔር የተቀበለው ሠራተኛ

14ስለ እነዚህ ነገሮች ማሳሰብህን አትተው፤ በቃላት እንዳይነታረኩ በእግዚአብሔር ፊት አስጠንቅቃቸው፤ ይህ ጥቅም የሌለው፣ የሚሰሙትንም የሚያፈርስ ነውና:: 15እንደ ማያፍርና የእውነትን ቃል በትክክል እንደሚያስረዳ የተመሠከረለት ሠራተኛ፣ ራስህን በእግዚአብሔር ፊት ልታቀርብ ትጋ:: 16እግዚአብሔርን ከማያስከብር ከንቱ ልፍለፋ ራቅ፤ በዚህ ነገር የተጠመዱ ሰዎች ከእግዚአብሔር እየራቁ ይሄዳሉና:: 17ትምህርታቸው እንደማይሽር ቍስል ይሠራጫል፤ ከእነዚህም መካከል ሄሜኔዎስና ፊሊጦስ ይገኛሉ፤ 18እነዚህም ከእውነት ርቀው የሚባዝኑ ናቸው:: እነርሱም ትንሣኤ ሙታን ከዚህ በፊት ሆኖአል እያሉ የአንዳንዶቹን እምነት ይገለብጣሉ:: 19ይሁን እንጂ፣ "ጌታ የእርሱ የሆኑትን ያውቃል፤" ደግሞም፣ "የጌታን ስም የሚጠራ ሁሉ ከክፋት ይራቅ" የሚል ማኅተም ያለበት የማይነቃነቅ የእግዚአብሔር መሠረት ቆሞአል::

20በአንድ ትልቅ ቤት ውስጥ የወርቅና የብር ዕቃ ብቻ ሳይሆን፣ የዕንጨትና የሸክላ ዕቃም ይኖራል፤ ከእነዚህ አንዳንዶቹ ለክብር፣ ሌሎቹም ላልከበረ አገልግሎት ይውላሉ:: 21እንግዲህ ማንም ራሱን ከእነዚህ ከጠቀስኋቸው ነገሮች ቢያነጻ ለክቡር አገልግሎት የሚውል፣ የተቀደሰ፣ ለጌታው የሚጠቅም፣ ለመልካም ሥራም ሁሉ የተሰናዳ ዕቃ ይሆናል::

22ከወጣትነት ክፉ ምኞት ሽሽ፤ በንጹሕ ልብ ጌታን ከሚጠሩት ጋርም ጽድቅን፣ እምነትን፣ ፍቅርንና ሰላምን ተከታተል:: 23ከማይረባና ትርጕም የለሽ ከሆነ ክርክር ራቅ፤ ምክንያቱም እነዚህ ጠብን እንደሚያስከትሉ ታውቃለህ:: 24የጌታም አገልጋይ ሊጣላ አይገባውም፤ ይልቁን ለሰው ሁሉ ገር፣ ለማስተማር ብቃት ያለው፣ ትዕግሥተኛም መሆን ይገባዋል፤ 25እውነትን ወደ ማወቅ

2፥5 1ቆሮ9፥25
2፥6 1ቆሮ9፥10
2፥8 ማቴ1፥1፤ ሐሥ2፥24፤ሮሜ2፥16፤ 16፥25
2፥9 ሐሥ9፥16፤ 21፥33፤ዕብ4፥12
2፥10 2ቆሮ1፥6፤ 4፥17፤ቈላ1፥24፤ ቲቶ1፥1፤1ጴጥ5፥10
2፥11 ሮሜ6፥2-11፤ 1ጢሞ1፥15
2፥12 ማቴ10፥33፤ ሮሜ8፥17፤1ጴጥ4፥13
2፥13 ሮሜ3፥3፤ 1ቆሮ1፥9
2፥14 ቍ23፤ 1ጢሞ1፥4፤6፥4፤ ቲቶ3፥9
2፥15 ኤፌ1፥13፤ ቈላ1፥5፤ያዕ1፥18
2፥16 1ጢሞ6፥20፤ ቲቶ3፥9
2፥17 1ጢሞ1፥20
2፥18 2ተሰ2፥2፤ 1ጢሞ1፥19፤6፥21
2፥19 ዘፀ33፥12፤ ዘኍ16፥5፤ኢሳ28፥16፤ ዮሐ10፥14፤1ቆሮ1፥2፤ 8፥3፤ገ4፥9
2፥20 ሮሜ9፥21
2፥21 2ቆሮ9፥8፤ ኤፌ2፥10፤2ጢሞ3፥17
2፥22 ሐሥ2፥21፤ 1ጢሞ1፥5፡14
2፥23 ቍ14
2፥24 1ጢሞ3፥2፡3
2፥25 1ጢሞ2፥4

2) የውድድሩን ሥርዐት የሚከተል ሯጭ 3) ተግቶ የሚሠራ ገበሬ

2፥6 *ከሰብሉ ለመጠቀም፤* እንደ መጀመሪያዎቹ ሁለቱ (እንደ ወታደር ቍ3-4 እና እንደ ሯጭ ቍ5) ከዚህ የምንማረው መሠረታዊ ትምህርት ከልብ የሚደረጉ ጥረቶች እንደሚያሸልሙ ነው:: ይህም ሽልማት በገንዘብ የሚተመን ስጦታ ብቻ ሳይሆን፣ በወንጌል ኀይል የተለወጠ ሕይወት በማየት የሚገኝ ደስታ ነው::

2፥8 *ከሙታን የተነሣውን፣ ከዳዊት ዘርም የሆነውን፤* የክርስቶስ ትንሣኤ አምላክ መሆኑን፣ ከዳዊት ዘር መምጣቱ ደግሞ ሰው መሆኑን ያሳያል፤ ሁለቱም የወንጌል መሠረታዊ እውነቶች ናቸው:: ክርስቶስ አምላክ እንደ መሆኑ መጠን ሞቱ እጅግ በጣም ከፍ ያለ ዋጋ አለው፤ ሰው እንደ መሆኑ መጠን ደግሞ በእኛ ምትክ ሊሆን ችሎአል::

2፥9 *እንደ ወንጀለኛ እስከ መታሰር ድረስ፤* ጳውሎስ የሚገደልበትን ቀን እንደሚጠባበቅ ግልጽ ነው (4፥6 ይመ)::

2፥10 *በክርስቶስ ኢየሱስ፤* የ1፥3 ማብ ይመ:: *ከዘላለም ክብር፤* የድነት የመጨረሻው ውጤት ነው:: *ለተመረጡት ስል ሁሉንም በመታገሥ እጸናለሁ፤* አምነው የእግዚአብሔር ምርጦች ስለሚሆኑት ድነት ከሆነ ማናቸውም መከራ ይኸን ያህል ሊከብድ አይችልም::

*2፥11-13፤* ይህ የክርስቲያኖች የመጀመሪያው መዝሙር ሳይሆን አይቀርም:: ጳውሎስ ለማስተማር የፈለገው ነጥብ፣ የክርስቶስ መሠቃየት ክብርን የሚያጐናጽፍ መሆኑን ነው::

2፥11 *የሚለው ቃል የታመነ ነው፤* የ1ጢሞ 1፥15 ማብ ይመ:: *ከእርሱ ጋር ከሞትን፣ ከእርሱ ጋር ደግሞ በሕይወት እንኖራለን፤* የግሪኩ አገላለጽ ክርስቶስ በመስቀል ላይ ስለ እኛ በሞተ ጊዜ እኛም ከእርሱ ጋር መሞታችንን ያሳስባል፤ ከዚህ የተነሣ ከእርሱ ጋር ለዘላለም የመኖር ዋስትና ተሰጥቶናል::

2፥12 *ብንጸና...እንነግሣለን* በትዕግሥትና በታማኝነት ጸንቶ በመከራና በፈተና ውስጥ ማለፍ ክርስቶስ በሚገለጥበት ጊዜ ሽልማት ያስገኛል:: *ብንክደው፤* ማቴ 10፥33 ይመ::

*2፥14-18፤* ከቁ 14-18 ላይ ካሉት ቃላት የምንረዳው፣ በዚህ ስፍራ የተጠቀሰው የኑፋቄ ትምህርት የመጀመሪያው የኖስትሳውያን ትምህርት ሲሆን፣ በ1ጢሞቴዎስና በቲቶ መልእክት ከተጠቀሰው ጋር ተመሳሳይ ነው (የ1ጢሞ 1፥3-11 ማብ እንዲሁም ከ1ዮሐንስ መግቢያ ላይ፣ "ኖስትሳውያት ትምህርት" የሚለውን ይመ):: የዚህ ኑፋቄ ትምህርት ሁለት መሪዎች፣ ሄሜኔዎስ (1ጢሞ1፥20 ይመ) እና ፊሊጦስ የአካል ትንሣኤን በመካድ፣ ምናልባት ትንሣኤ የሚሆነው በመንፈስ ነው ይሉ ይሆናል (ይህ ዐይነቱ ስሕተት በ1ቆሮ15፥12-19 ላይ ተጠቅሶ ይገኛል):: የኖስትሳውያን ትምህርት ትንሣኤን ቃል በቃል ሳይሆን፣ በተራዛሚ ትርጕም ነው የሚፈቱት::

2፥15 *የእውነትን ቃል፤* ወንጌልን ማለት ነው::*ጥረት አድርግ፤* 4፥9፡21 ይመ::

2፥19 *ማኅተም ያለበት፤* ቤተ ክርስቲያን የእግዚአብሔር ናት፤ እርሱም በሚያስተማምን ሁኔታ ይጠብቃታል (የኤፌ1፥13 ማብ ይመ):: *የማይነቃነቅ የእግዚአብሔር መሠረት፤* እርሷም ዐምድና መሠረት ሆና እውነትን አጽንታ የያዘች ቤተ ክርስቲያን ናት (1ጢሞ 3፥15):: የሄሜኔዎስና የፊሊጦስ የኑፋቄ ትምህርት በአካባቢው ቢኖርም ቤተ ክርስቲያን የማትነቃነቅ የእግዚአብሔር መሠረት መሆኗን ለማወቅ ጢሞቴዎስ መበርታት አለበት:: በዚህች መሠረት ላይ ሁለት ነገሮች ተቀርጸዋል፤ አንዱ ለቤተ ክርስቲያን የተሰጣትን ዋስትና ያመለክታል ("ጌታ የእርሱ የሆኑትን ያውቃል"፤ በመጽሐፍ ቅዱስ "ማወቅ" የሚለው ቃል አብጠርጥሮ ማወቅን የሚያመለክት ነው):: ሌላው ግን ለሰው የተሰጠውን ኀላፊነት በአጽንዖት ያሳያል ("የጌታን ስም የሚጠራ ሁሉ ከክፋት ይራቅ")::

2፥22 *ከወጣትነት፤* የ1ጢሞ 4፥12 ማብ ይመ::

ይደርሱ ዘንድ፣ ስግዚስብሔር ንስሓን እንደሚሰጣቸው ተስፋ በማድረግ የሚቃወሙትን በየዋህነት የሚያቃና መሆን ይኖርበታል፤ 26ይኸውም ወደ አእምሮአቸው ይመለሳሉ፤ ፈቃዱን ሊያስፈጽማቸው ምርኮኛ አድርጎ ከያዛቸው ከዲያብሎስ ወጥመድም ያመልጣሉ በማለት ነው።

## ክሕደት በመጨረሻዎቹ ቀናት

**3** ነገር ግን በመጨረሻው ዘመን የሚያስጨንቅ ጊዜ እንደሚመጣ ይህን ዕወቅ። 2ሰዎች ራሳቸውን የሚወዱ ይሆናሉ፤ ገንዘብን የሚወዱ፣ ትምክህተኞች፣ ትዕቢተኞች፣ ተሳዳቢዎች፣ ለወላጆቻቸው የማይታዘዙ፣ የማያመሰግኑ፣ ቅድስና የሌላቸው፣ 3ፍቅር የሌላቸው፣ ለዕርቅ የማይሸነፉ፣ ሐሜተኞች፣ ራሳቸውን የማይገዙ፣ ጨካኞች፣ መልካም የሆነውን የማይወዱ፣ 4ከዳተኞች፣ ችኩሎች፣ በከንቱ በትዕቢት የተወጠሩ፣ ከስግዚስብሔር ይልቅ ተድላን የሚወዱ ይሆናሉና። 5ሃይማኖታዊ መልክ አላቸው፤ ኀይሉን ግን ክደዋል። ከእነዚህ ራቅ።

6እነርሱም በየቤቱ ሾልከው እየገቡ የኀጢአት ብዛት የተጫናቸውን፣ በተለያዩ ክፉ ምኞት ውስጥ ገብተው የሚዋልሉ መንፈሰ ደካማ ሴቶችን የሚያጠምዱ ናቸው፤ 7እንደነዚህ ያሉ ሴቶች ሁልጊዜ ይማራሉ፤ ነገር ግን እውነትን ወደ ማወቅ ፈጽሞ ሊደ ርሱ አይችሉም። 8ኢያኔስና ኢያንበሬስ ሙሴን እንደ ተቃወሙት፣ እነዚህም አእምሮአቸው የጠፋባቸውና ከእምነት የተጣሉ ሰዎች ደግሞ እውነትን ይቃወማሉ። 9ይሁን እንጂ አይሳካላቸውም፤ ምክንያቱም የእነዚያ ሰዎች ሞኝነት እንደ ተገለጠ ሁሉ፣ የእነዚህም ለሁሉ ግልጽ ይሆናል።

## ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ የሰጠው ዐደራ

10አንተ ግን ትምህርቴን፣ አካሄዴን፣ ዐላማዬን፣ እምነቴን፣ ትዕግሥቴን፣ ፍቅሬንና፣ ጽናቴን ሁሉ ታውቃለህ፤ 11ስደቴንና መከራዬን፣ በአንጾኪያና በኢቆንዮን፣ በልስጥራንም የደረሰብኝን ሁሉ፣ የታገሥሁትንም ስደት ታውቃለህ፤ ጌታ ግን ከእነዚህ ሁሉ አዳነኝ። 12በእርግጥም በክርስቶስ ኢየሱስ በእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት መኖር የሚወዱ ሁሉ ይሰደዳሉ። 13ክፉዎችና አታላዮች ግን እየሳቱና እየሳቱ፣ በክፋትም ላይ ክፋት እየጨመሩ ይሄዳሉ። 14አንተ ግን በተማርኸውና በተረዳኸው ጽና፤ ይህን ከማን እንደ ተማርኸው ታውቃለህና፤ 15ከሕፃንነትህም ጀምረህ፣ በክርስቶስ ኢየሱስ በማመን መዳን የሚገኝበትን ጥበብ ሊሰጡህ የሚችሉትን ቅዱሳት መጻሕፍትን ዐውቀሃል። 16ቅዱሳት መጻሕፍት ሁሉ የስግዚስብሔር መንፈስ ያለባቸው ናቸው፤ ለማስተማር፣ ለመገሠጽ፣ ለማቅናት በጽድቅም መንገድ ለመምከር ይጠቅማሉ፤ 17ይኸውም የስግዚስብሔር ሰው ለመልካም ሥራ ሁሉ ብቁ ሆኖ እንዲገኝ ነው።

**4** በስግዚስብሔር ፊት እንዲሁም በሕያዋንና በሙታን ሊፈርድ ባለው በክርስቶስ ኢየሱስ ፊት፣ መገለጡንና መንግሥቱን በማሰብ ይህን ዐደራ እልሃለሁ፤ 2ቃሉን ስበክ፤ ጊዜው ቢመችም ባይመችም ዝግጁ ሁን፤ በታላቅ ትዕግሥትና በማስተማር አቅና፤ ገሥጽ፤ አበረታታም። 3ምክንያቱም ሰዎች ትክክለኛ የሆነውን ትምህርት የማይቀበሉበት ጊዜ ይመጣል፤ ከዚህ ይልቅ ለገዛ ምኞቶቻቸው የሚስማማውን፣ የሚያሳክክ ጆሮአቸው ሊሰማ የሚፈልገውን እንዲነግሯቸው በዙሪያቸው ብዙ አስተማሪዎችን ይሰበስባሉ። 4እውነትን ከመስማት ጆሮአቸውን ይመልሳሉ፤

2፥26 1ጢሞ3፥7
3፥1 1ጢሞ4፥11 2ጴጥ3፥3
3፥2 ሮሜ1፥30፤ 1ጢሞ3፥3፤ 2ጴጥ2፥10-12
3፥4 መዝ25፥3፤ 1ጢሞ3፥6፤6፥4
3፥5 ሮሜ16፥17፤ 1ጢሞ2፥2
3፥6 ይሁ 4
3፥7 1ጢሞ2፥4
3፥8 ዘፀ7፥11፤ ሐሥ13፥8፤1ጢሞ6፥5
3፥9 ዘፀ7፥12፤ 8፥18፤9፥11
3፥10 1ጢሞ4፥6
3፥11 መዝ34፥19፤ ሐሥ13፥14:51፤ 14፥6፤ሮሜ15፥31፤ 2ቆሮ11፥23-27
3፥12 ሐ15፥20፤ ሐሥ14፥22
3፥13 ማር13፥5፤ 2ጢሞ2፥16
3፥14 2ጢሞ1፥13
3፥15 ዘዳ4፥6፤ መዝ119፥98:99፤ ዮሐ5፥39፤2ጢሞ1፥5
3፥16 ዘዳ29፥29፤ ሮሜ4፥23:24፤ 2ጴጥ1፥20
3፥17 1ጢሞ6፥11፤ 2ጢሞ2፥21
4፥1 ቆላ8፤ ሐሥ10፥42፤ 1ጢሞ5፥21፤6፥13:14
4፥2 ገላ6፥6፤ 1ጢሞ4፥13፤5፥20፤ ቲቶ1፥13፤2፥15
4፥3 ኢሳ30፥10፤ 1ጢሞ1፥10
4፥4 1ጢሞ1፥4

3፥1 *በመጨረሻው ዘመን፤* ክርስቶስ ወደዚህ ዓለም ከመጣበት ጊዜ ጀምሮ ያለውን የመሲሑን ዘመን ያመለክታል (የሐሥ 2፥17፤ 1ጢሞ 4፥1፤ ዕብ 1፥1፤ 1ጴጥ 1፥20፤ 1ዮሐ 2፥18 ማብ ይመ)፤ ጢሞቴዎስ በዘመኑ ከነበሩት ከማያምኑና ከማይታመኑ ሰዎች እንዲርቅ ጳውሎስ የሰጠው ትእዛዝ፣ "በመጨረሻው ዘመን" የሚለው ሐረግ ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት ብቻ እንደማይናገር ይገልጻል (ቊ 5)።

3፥6 *መንፈሰ ደካማ ሴቶች፤* ለምኞታቸው የተሸነፉ፣ ለኑፋቄ ትምህርት መምህራን የተገዙ፣ ዘወትር የሚማሩ (ቊ 7)፣ ዳሩ ግን ወደ ክርስቶስ ድኅነት የማይመጡና በኀጢአታቸውም እግዚአብሔርን የሚያሳዝኑ ወላዋይ ሴቶች ናቸው።

3፥8 *ኢያኔስና ኢያንበሬስ፤* የሁለቱም ስም በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት አልተጠቀሱም፤ በአይሁድ ትውፊት መሠረት ግን ሙሴን የተቃወሙ የግብፅ ቤተ መንግሥት አስማተኞች እንደነበሩ ይነገራል (ዘጸ 7፥11 እና ማብ ይመ)።

3፥11 *በአንጾኪያና በኢቆንዮን፣ በልስጥራንም፤* ሦስቱም ከተሞች በገላትያ አውራጃ ይገኛሉ፤ ጳውሎስ በመጀመሪያውና በሁለተኛው የወንጌል ጕዞው ጐብኝቶአቸዋል (ሐሥ13፥14-14:23፤ 16፥1-6)፤ ጢሞቴዎስ ከልስጥራን የመጣ በመሆኑ እዚያ በጳውሎስ ላይ ከመጀመሪያው ጀምሮ ስለ ደረሰበት መከራ ያውቃል። *ጌታ ግን ከእነዚህ ሁሉ አዳነኝ፤* በድንጋይ ተወግሮ ከመሞት እንኳ ማለት ነው (ሐሥ 14፥19-20)።

*3፥12፤* በአዲስ ኪዳን ተደጋግሞ የተጠቀሰ መመሪያ ነው (ማቴ 10፥22፤ ሐሥ 14፥22፤ ፊል 1፥29፤ 1ጴጥ 4፥12 ይመ)። *በክርስቶስ፤* የ1፥13 ማብ ይመ።

3፥14 *ከማን እንደተማርኸው፤* ሐረጉ ጳውሎስን፣ እንዲሁም የጢሞቴዎስን እናትና አያት ሊያመለክት ይችላል (1፥5)።

3፥15 *ከሕፃንነትህም ጀምረህ…ቅዱሳት መጻሕፍትን ዐውቀሃል፤* አንድ አይሁዳዊ ዕድሜው አምስት ዓመት ሲሞላው ብሉይ ኪዳንን ማጥናት ይጀምራል። እናቱና አያቱ ጢሞቴዎስን በቤት ማስተማር የጀመሩት ግን ዕድሜው እዚህ ከመድረሱ በፊት ነበር።

3፥16 *ቅዱሳት መጻሕፍት ሁሉ፤ ቃሉ አበክሮ መግለጽ የፈለገው* የብሉይ ኪዳንን መጻሕፍት ነው፤ ምክንያቱም በወቅቱ አንዳንድ የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት አልተጻፉም ነበር (ጥቂት የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ወይም ጽሑፎች ግን ከብሉይ ኪዳን ቅዱሳት መጻሕፍት ጋር እኩል ተደርገው እንዲቈጠሩ መደረጋቸውን የሚጠቍሙ ንባባት አሉ፤ (1ጢሞ 5፥18፤ 2ጴጥ3፥15-16 ይመ)። *የእግዚአብሔር መንፈስ ያለባቸው፤* የተጻፈው ሁሉ ሕጸጽ የሌለበትና እውነተኛ የእግዚአብሔር ቃል ይሆን ዘንድ ቅዱሳት መጻሕፍትን በመጻፍ ረገድ የእግዚአብሔር ተሳትፎ ንቁና ኀያል እንደ ነበር ጳውሎስ ያረጋግጣል (2ጴጥ 1፥20-21 እና ማብ ይመ)።

4፥1 *ዐደራ እልሃለሁ፤* ጳውሎስ ይህን ኀላፊነት ለጢሞቴዎስ የሰጠው በእግዚአብሔር አብ ፊትና በሰዎች ሁሉ ላይ በሚፈርደው በክርስቶስ ኢየሱስ ፊት እንደ ሆነ እንዲያውቅ በማሳሰብ ነው። በተጨማሪም ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአትና ወደ ፊት ስለሚመጣው የእግዚአብሔር መንግሥት እየገለጸ ከሁሉ በበለጠ ሁኔታ ትኵረት እንዲሰጠው ይጽፍለታል።

4፥2 *ዝግጁ ሁን፤* ለመምከርም ይሁን ለመገሠጽ ወይም ለማጽናናት፣ በማንኛውም ረገድ አስፈላጊ የሆነውን ቃል ለመናገር የተዘጋጀ እንዲሆን ይመክረዋል።

4፥3 *ትክክለኛ የሆነውን ትምህርት፤* የቲቶ 1፥9 ማብ ይመ። *የሚያሳክክ ጆሮአቸው፤* ለክፉ ምኞቶቻቸው እንዲገዙ በሚደረግ ቃል መታከክ የሚፈልግ ጆሮዎችን ነው።

4፥4 *ተረት፤* የ1ጢሞ 1፥4 ማብ ይመ።

ወደ ተረትም ዘወር ይላሉ። [5]አንተ ግን በሁኔታዎች ሁሉ የረጋህ ሁን፤ መከራን ታገሥ፤ የወንጌል ሰባኪን ተግባር አከናውን፤ አገልግሎትህን ፈጽም።

[6]እኔ እንደ መጠጥ ቍርባን መሥዋዕት ለመፍሰስ ተቃርቤአለሁ፤ ተለይቼ የምሄድበት ጊዜ ደርሶአል። [7]መልካሙን ገድል ተጋድያለሁ፤ ሩጫውን ጨርሻለሁ፤ ሃይማኖትንም ጠብቄአለሁ። [8]ወደ ፊት የጽድቅ አክሊል ተዘጋጅቶልኛል፤ ይህንም ጻድቅ ፈራጅ የሆነው ጌታ በዚያ ቀን ለእኔ ይሰጠኛል፤ ደግሞም ለእኔ ብቻ ሳይሆን፣ የእርሱን መገለጥ ለናፈቁ ሁሉ ነው።

## የጳውሎስ ማሳሰቢያ

[9]በቶሎ ወደ እኔ ለመምጣት የተቻለህን ሁሉ አድርግ፤ [10]ዴማስ ይህን ዓለም ወዶ፣ ትቶኝ ወደ ተሰሎንቄ ሄዶአልና። ቄርቂስ ወደ ገላትያ፣ ቲቶ ወደ ድልማጥያ ሄደዋል፤ [11]ከእኔ ጋር ያለው ሉቃስ ብቻ ነው። ማርቆስ በአገልግሎቴ ስለሚረዳኝ ከአንተ ጋር ይዘኸው ና። [12]ቲኪቆስን ወደ ኤፌሶን ልኬዋለሁ። [13]ስትመጣ በጢሮአዳ ከአክርጳ ዘንድ የተውሁትን በርኖስ፣ ጥቅልል መጻሕፍቱን በተለይም የብራና መጻሕፍቱን አምጣልኝ።

[14]አንጥረኛው እስክንድሮስ ብዙ ጕዳት አድርሶብኛል፤ ጌታ ግን የእጁን ይሰጠዋል። [15]መልእክታችንን እጅግ ተቃውሞአልና፣ አንተም ከእርሱ ተጠንቀቅ።

[16]በተከሰስሁበት ነገር የመጀመሪያ መከላከያዬን ሳቀርብ ማንም ሊያግዘኝ አልመጣም፤ ነገር ግን ሁሉ ትተውኝ ሄዱ። ይህንም አይቍጠርባቸው። [17]ነገር ግን መልእክቱ በእኔ አማካይነት በሙላት እንዲሰበክና አሕዛብ ሁሉ እንዲሰሙት ጌታ በአጠገቤ ቆሞ አበረታኝ፤ ከአንበሳም መንጋጋ አዳነኝ። [18]ጌታ ከክፉ ነገር ሁሉ ያድነኛል፤ ወደ ሰማያዊው መንግሥቱም በሰላም ያደርሰኛል፤ ለእርሱ ከዘላለም እስከ ዘላለም ክብር ይሁን፤ አሜን።

## የስንብት ሰላምታ

[19]ለጵርስቅላና[ሀ] ለአቂላ፣ ለሄኔሲፎሩም ቤተ ሰዎች ሰላምታ አቅርብልኝ። [20]ኤርስጦስ በቆሮንቶስ ቀርቶአል፤ ጥሮፊሞስም ስለ ታመመ በሚሊጢን ትቼዋለሁ። [21]ከክረምት በፊት እዚህ ለመምጣት የተቻለህን አድርግ። ኤውግሎስና ጱዴስ እንዲሁም ሊኖስ፣ ቅላውዲያና ወንድሞች ሁሉ ሰላምታ ያቀርቡልሃል።

[22]ጌታ ከመንፈስህ ጋር ይሁን። ጸጋ ከእናንተ ጋር ይሁን።

4፥5 ሐሥ21፥8፤ ኤፌ4፥11፤ 2ጢሞ1፥8፤2፥3
4፥6 ዘኍ15፥1-12፤ 28፥7:24፤ፊል1፥23፤ 2፥17
4፥7 ሐሥ20፥24፤ 1ቆሮ9፥24፤1ጢሞ1፥18
4፥8 1ቆሮ9፥25፤ ቈላ1፥5፤1ጢሞ6፥14፤ 2ጢሞ1፥12፤ 1ጴጥ1፥4
4፥9 ቲቶ3፥12 ቍ21፤
4፥10 ሐሥ16፥6፤ 17፥1፤2ቆሮ2፥13፤ ቈላ4፥14፤ፊሞ24፤ 1ዮሐ2፥15
4፥11 ሐሥ12፥12፤ ቈላ4፥14፤ፊሞ24፤ 2ጢሞ1፥15
4፥12 ሐሥ18፥19፤20፥4
4፥13 ሐሥ16፥8
4፥14 መዝ28፥4፤ 109፥20፤ሐሥ19፥33፤ ሮሜ2፥6፤12፥19፤ 1ጢሞ1፥20
4፥16 ሐሥ7፥60
4፥17 1ሳሙ17፥37፤ መዝ22፥21፤ዳን6፥22፤ ሐሥ9፥15፤23፥11፤ 1ቆሮ15፥32፤ፊል4፥13
4፥18 ቍ1፤ መዝ121፥7፤ ሮሜ 11፥36፤ 2ጴጥ2፥9
4፥19 ሐሥ18፥2፤ 2ጢሞ1፥16 4፥20 ሐሥ19፥22፤ 20፥4:15፡ 17፤21-29 4፥21 ቍ9፤ ቲቶ3፥12 4፥22 ገላ6፥18፤ ቈላ4፥18

[ሀ] 19 ግሪኩ *ጵርስቃ* ይላል።

4፥6 *መጠጥ ቍርባን መሥዋዕት፤* በመሠዊያው ዙሪያ የሚፈስን የወይን ጠጅ መሥዋዕት ነው (ዘኍ 15፥1-12፤ 28፥7:24 ይመ)። ጳውሎስ ሕይወቱን መሥዋዕት አድርጎ ለክርስቶስ የሚያፈስበት ጊዜ መቅረቡን ለማመልከት የተጠቀመበት አገላለጽ ነው (ፊል 2፥17 ይመ)። *ተለይቼ የምሄድበት ጊዜ፤* የመሞቻውን ቅርበት ያሳያል (ከፊል1፥23 ጋር ያነጻጽሩ)።

*4፥7፤* እዚህ ላይ ጳውሎስ በሐዋርያነት የደከመበትን የሠላሳ ዓመት የሥራ ፍሬ ወደ ኋላ ተመልሶ ይመለከታል (በግምት ከ36-66 ዓ.ም.)። በውድድር ገብቶ ድልን እንደ ተቀዳጀ ሯጭ (መልካሙን ገድል ተጋድያለሁ) ጳውሎስም ሩጫውን በድል ተወጥቶታል፤ እምነቱን ጠብቆአል፤ ለክርስትና ትምህርትም እንደሚገባ ታዞአል (2፥5 ይመ)። ወይም በመልእክታተ ምጋቤ ትክክለኛ አስተምህሮ መሠረት ከታየ፣ "እምነት" የክርስትና እውነት ውጤት መሆኑን ያመለክታል። ጳውሎስ እነዚህን ጠብቆአል።

4፥8 *የጽድቅ አክሊል፤* አሁንም ጳውሎስ ተመሳሳይ ተለዋጭ ዘይቤን በመጠቀም በውድድር ላሸነፈ ሰው የሚሰጠውን ዕቅፍ አበባ እዚህ ላይ ይጠቅሰዋል (1ቆሮ 9፥25)። ይህንም፦ (1) የጻደቀች ነፍስ በሽልማት የምትቀዳጀውን አክሊል (2) ጽድቅን ያካተተውን አክሊል፣ (3) ጻድቁ ፈራጅ፣ በጽድቅ ሰው የሚሰጠውን አክሊል ሊያመለክት ይችላል። *በዚያ ቀን፤* በክርስቶስ ዳግም ምጽአት።

4፥10 *ቄርቂስ፤* ከዚህ ስፍራ በስተ ቀር በየትኛውም የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ ስሙ አልተጠቀሰም። *ገላትያ፤* የትንሹ እስያ ሰሜናዊ ክፍል (ጋውል) ወይም በአሁኑ ጊዜ የመካከለኛው ቱርክ የሚገኝበት ናት (የገላ 1፥2 ማብ ይመ)። *ቲቶም፤ ወደ ድልማጥያ፤* ከቲቶ መግቢያ "ተደራሲያኑ" የሚለውን ይመ። *ድልማጥያ፤* የዩጎዘላቪያ ክፍለ ሀገር የነበረችውና የአሁኗ አልባኒያ በቅዱሳት መጻሕፍት እልዋሪቆን (ሮም 15፥19) በመባልም ትታወቃለች።

4፥11 *ማርቆስ፤* ዮሐንስ ማርቆስ፣ ጳውሎስንና በርናባስን በመጀመሪያ የወንጌል ጕዞአቸው ወቅት ጥሎአቸው ሄዶ ስለነበር (ሐሥ 13፥13)፣ ጳውሎስ በሁለተኛው የወንጌል ጕዞ ማርቆስን ይዞ ለመሄድ ባለመፈለጉ በርናባስ ከጳውሎስ ተለይቶ ማርቆስን ይዞ ወደ ቆጵሮስ ሄደ (ሐሥ 15፥36-41)። በመጨረሻ ግን ማርቆስ፣ ጳውሎስ መጀመሪያ በሮም በታሰረበት ወቅት (ቈላ 4፥10፤ ፊል 24) እንዲሁም ጢሞቴዎስ ማርቆስን ይዞ ወደ ሮም እንዲመጣ ጳውሎስ በጠየቀበት ወቅት ሁሉ አብሮት በመሆን ወዳጅነቱን አሳይቶአል።

4፥13 *አክርጳ፤* በሌላ ሥፍራ አልተጠቀሰም። *በርኖስ፤* ሙቀት የሚሰጥ የብርድ መከላከያ (መግቢያው ይመ) ነው። በርኖስ፣ እጅጌ የሌለው ከባድና ወፍራም ሆኖ መካከሉ ላይ የራስ ማስገቢያ ቀዳዳ ያለው ካባ መሰል ልብስ ነው። *ጥቅልል መጻሕፍቱን፣ በተለይም የብራና መጻሕፍቱን፤* ጥቅል መጻሕፍቱ (የዘፀ 17፥14 ማብ ይመ) ከፓፒረስ፣ የብራና መጻሕፍቱ ደግሞ ከእንስሳት ቆዳ የተሠሩ ናቸው። ብራናው የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ሊሆኑ ይችላሉ።

4፥14 *አንጥረኛው እስክንድሮስ፤* በ1ጢሞ 1፥20 ላይ የተጠቀሰው እስክንድሮስ ሳይሆን አይቀርም።

4፥16 *የመጀመሪያ መከላከያዬን፤* ጳውሎስ፣ በወቅቱ ችሎት ቀርቦ መልስ የሰጠበት የመጀመሪያው ክስ እንጂ በመጀመሪያው እስር ወቅት ይግባኝ ብሎ ወደ ሮም የመጣበት ጕዳይ አይደለም (ሐሥ 28)።

4፥17 *መልእክቱ በእኔ አማካይነት በሙላት እንዲሰበክና፤* በዚህ ተስፋ በሚያስቈርጥ ሁኔታ ውስጥ እንኳ ጳውሎስ ለቄሳርን ችሎት ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ አዳኝነት ለመመስከር ተጠቅሞበታል። *ከአንበሳም መንጋጋ አዳነኝ፤* ጳውሎስ በአንበሳ ጕድጓድ ውስጥ ሊጣል አይችልም ዳሩ ግን ፍርድ ቤት ቀርቦ የሰጠው መልስ ከፉ እንዳላመጣበት ለመግለጽ የተጠቀመበት ዘይቤያዊ አነጋገር ነው።

4፥18 *ጌታ ከክፉ ነገር ሁሉ ያድነኛል፤* ጳውሎስ ከጥቂት ጊዜ በኋላ እንደሚሞት በቍ 6 ላይ ተናግሮአል። ስለዚህ እዚህ ላይ የተናገረው ክፉ ነገር መንፈሳዊ እንጂ ሥጋዊ አይደለም።

4፥19 *ሄኔሲፎሩ፤* የ1፥16 ማብ ይመ።

4፥20 *ኤርስጦስ፤* የሮሜ 16፥23 ማብ ይመ። *ሚሊጢን፤* ከኤፌሶን በስተ ደቡብ 80 ኪ. ሜትር ርቃ በትንሿ እስያ ጠረፍ ላይ የምትገኝ የባሕር ወደብ ናት።

4፥21 *ሊኖስ፤* ጴጥሮስና ጳውሎስ ከሞቱ በኋላ በሮም የቤተ ክርስቲያን እረኛ እንደ ነበረ በትውፊት ይነገራል።

4፥22 *ጸጋ፤* የዮና 4፥2፤ ገላ 1፥3፤ ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ። *ከእናንተ፤* በጢሞቴዎስ መጨረሻ ላይ ተጠቅሶ እንደምናገኘው፣ ደብዳቤው በግል ብቻ ሳይሆን በማኅበር እንዲነበብ ታስቦ የተጻፈ በመሆኑ "ከመንፈስህ" የሚለው ቃል ግን ጢሞቴዎስን ብቻ ያመለክታል። ጳውሎስ የሚሞትበት ጊዜ እየተቃረበ በመጣበት ጊዜ ገና ወጣትና ድንጉጥ ለሆነው ለወዳጁ ጢሞቴዎስ ከሰጠው ከፍተኛ ዐደራ አንጻር ሲታይ ጢሞቴዎስን ማበረታቱ አማራጭ የሌለው ጕዳይ መሆኑ ግልጽ ነው።

# የሐዋርያው ጳውሎስ መልእክት
# ወደ ቲቶ

## መግቢያ

በገጽ 1835 ላይ "መልእክታተ ምጋቢ" የሚለውን ይመ::

### ጸሓፊው

የመልእክቱ ጸሓፊ ጳውሎስ ነው (ከ1ኛ ጢሞቴዎስ መግቢያ፤ "ጸሓፊው" የሚለውን ይመ)::

### የመልእክቱ ተደራሲ

ይህ መልእክት የተጻፈው ጳውሎስ ወደ ጌታ ካመጣቸው ሰዎች መካከል አንዱ ለሆነውና የጳውሎስን አገልግሎት ይደግፍ ለነበረው ለቲቶ ነው:: ጳውሎስ በኢየሩሳሌም ከሚገኙ የቤተ ክርስቲያን መሪዎች ጋር ስለ ወንጌል ለመነጋገር ከአንጾኪያ ወደ ኢየሩሳሌም በሄደ ጊዜ (2ጢሞ22፥8) ቲቶን ይዞ ሄዶ ነበር (ገላ2፥1-3):: ቲቶ ከአሕዛብ ወገን ሆኖ ሳለ ሳይገረዝ ክርስቲያን ነው ብሎ እርሱን መቀበሉ የጳውሎስን አቋም የሚያመለክት ነው (ገላ2፥3-5):: በሐዋርያት ሥራ ውስጥ አንድ ጊዜም እንኳ ስሙ ያልተነሣውና በሌሎች የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ግን ዐሥራ ሦስት ጊዜ ስሙ የተጠቀሰው ቲቶ፣ በሦስተኛው የጳውሎስ የወንጌል ጉዞ ወቅት፣ በኤፌሶን የወንጌል ሥራ ውስጥ ተካፋይ ነበር:: በመቀጠልም፣ ጳውሎስ በቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን የነበረውን አገልግሎት ያጠናክር ዘንድ ቲቶን ልኮታል (የ2ቆሮ2፥12-13፤ 7፥5-6፤8፥6 ማብ ይመ)::

ጳውሎስ ከመጀመሪያ የሮም እስራቱ (ሐሥ28) ከተፈታ በኋላ፣ ከቲቶ ጋር ለአጭር ጊዜ በቀርጤስ አገልግሎአል (1፥5)፤ ቀጥሎም አንዳንድ የተጀመሩ ሥራዎችን ቲቶ እንዲያጠናቅቅ በቀርጤስ እንዲቈይ አደረገው (1፥5፤2፥15፤3፥12-13):: ቲቶን የሚተካው ሰው በስፍራው ከደረሰ በኋላ (3፥12)፣ በምዕራባዊ የግሪክ ጠረፍ ኒቆጵልዮን ወደምትባል ወደብ እንዲመጣና እንዲያገኘው ጳውሎስ ቲቶን ይጠይቃል:: ቲቶ ግን ወደ ድልማጥያ (የአሁንዋ ዩጐዝላቪያ፤ የ2ጢሞ 4፥10 ማብ ይመ) ለአገልግሎት ሄደ፤ ይህም በአዲስ ኪዳን ስለ ቲቶ የተነገረ የመጨረሻ ቃል ነው፤ በአጠቃላይ ቲቶ የተሰጠውን ኀላፊነት ስንመለከት ኀላፊነቱን መወጣት የሚችል ብቁ መሪ ነበር::

### ቀርጤስ

በሜድትራኒያን ባሕር ላይ ከሚገኙት ታላላቅ ደሴቶች መካከል አራተኛ የሆነችው ቀርጤስ፣ በኤጂያን ባሕር ላይ በስተ ደቡብ በኩል ትገኛለች (የ1ሳሙ30፥14 ማብ ይመ፤ በሐሥ27፥7-13 ላይ ካለው የጳውሎስ ገጠመኝ ጋር ያነጻጽሩ):: በአዲስ ኪዳን ዘመን በቀርጤስ ከፍተኛ የሥነ ምግባር ብልሹነት ይታይ ነበር፤ አጭበርባሪነት፣ ሆዳምነትና ስንፍና በሕዝቡ ዘንድ የተለመደ ነበር (1፥12)::

### ዐላማው

የክርስትናን ሃይማኖት ወደ ቀርጤስ ሰዎች ያመጣው ጳውሎስ እንደሆነ ግልጽ ነው፤ ይህም ጳውሎስና ቲቶ ቀርጤስን በጐበኙበት ጊዜ ሳይሆን አይቀርም፤ ከዚያም ቲቶ በቀርጤስ የነበረውን የቤተ ክርስቲያንን ሥራ እንዲያደራጅ ጳውሎስ ትቶት ሄደ:: ጳውሎስ ይህን መልእክት የላከው በቀርጤስ በኩል በሚወስደው መንገድ በጉዞ ላይ በነበሩት (3፥13) በዜማስና በአጵሎስ እጅ ነበር፤ መልእክቱም ቲቶ በወቅቱ የተነሳበትን ተቃውሞ መቋቋም የሚችልበትን ሥልጣንና መመሪያ (1፥5፤2፥1:7-8:15፤3፥9)፣ ስለ እምነትና ስለ ክርስቲያን ምግባር እንዲሁም ስለ ሐሰት ትምህርት ማስጠንቀቂያ ነበር፤ በተጨማሪም ጳውሎስ ለቲቶ ስላለው የወደ ፊት ዕቅድ ጽፎለታል (3፥12)::

### መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ

በዚህ ጊዜ ጳውሎስ ገና ወደ ኒቆጵልዮን ስላልደረሰ (3፥12) ይህን መልእክት የጻፈው ከቆሮንቶስ ሳይሆን አይቀርም:: ይህን መልእክት የጻፈው ከመጀመሪያው የሮም እስራቱ በኋላ (ሐሥ28) ማለትም ከ63 እስከ 65ዓም ባለው ጊዜ ወይም ወደ እስጳንያ ሊያደርገው ካሰበው ጉዞ በኋላ ጽፎ ከሆነ ደግሞ ከ65 ዓ.ም. በኋላ ሊሆን ይችላል::

### የመልእክቱ ልዩ ባሕርይ

ይህ መልእክት በቀርጤስ በነበረው የሐሰት ትምህርት አንጻር የተጻፈ ሲሆን ይኸውም፣ "መልካም የሆነውን ማድረግ" (1፥16፤2፥7:14፤3፥1:8:14) በሚለው የክርስትና መሠረታዊ አስተምህሮ (2፥11-14፤ 3፥4-7) ላይ የተመሠረተ ነው::

### አስተዋፅኦ

1. ሰላምታ (1፥1-4)
2. ስለ ቤተ ክርስቲያን ሽማግሌዎች (1፥5-9)
   ሀ. ጳውሎስ ቲቶን በቀርጤስ የተወበት ምክንያት (1፥5)

ለ. የቤተ ክርስቲያን ሽማግሌዎች መመዘኛ(1፥6-9)
3. ስለ ሐሰት መምህራን (1፥10-16)
4. በማኅበረ ምእምናን መካከል የተለያዩ ቡድኖች (ም2)
   ሀ. ለተለያዩ ቡድኖች የተሰጠ መመሪያ (2፥1-10)
   ለ. የክርስትና ኑሮ መሠረት (2፥11-14)
   ሐ. የቲቶ ኀላፊነት (2፥15)
5. በአጠቃላይ ስለ አማኞች (3፥1-8)
   ሀ የዜግነት ግዴታ (3፥1-2)
   ለ ለእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት አነሣሽ ምክንያት (3፥3-8)
6. ለመንፈሳዊ ስሕተት የተሰጠ ምላሽ (3፥9-11)
7. ማጠቃለያ (3፥12-15)

# 1

¹የእግዚአብሔርን ምርጦች እምነትና ወደ እውነተኛ መንፈሳዊነት የሚመራውን የእውነት ዕውቀት ለማሳደግ የእግዚአብሔር ባሪያና የኢየሱስ ክርስቶስ ሐዋርያ የሆነው ጳውሎስ፤ ²እምነቱና ዕውቀቱ የተመሠረቱትም የማይዋሸው አምላክ ከዘመናት በፊት በገባው የዘላለም ሕይወት ተስፋ ላይ ነው:: ³እርሱ በወሰነውም ጊዜ በአዳኛችን በእግዚአብሔር ትእዛዝ ለእኔ ዐደራ በተሰጠኝ ስብከት በኩል ቃሉን ይፋ አደረገ::

⁴የጋራችን በሆነው እውነተኛ እምነት ልጄ ለሆነው ለቲቶ፤

ከእግዚአብሔር አብ፣ ከአዳኛችንም ከክርስቶስ ኢየሱስ ጸጋና ሰላም ይሁን::

## ቲቶ በቀርጤስ የነበረው ኀላፊነት

⁵አንተን በቀርጤስ የተውሁህ ገና ያልተስተካከለውን ነገር እንድታስተካክልና ባዘዝሁህ መሠረት በየከተማው ሽማግሌዎችን እንድትሾም ነው:: ⁶ሽማግሌ ነቀፋ የሌለበት፣ የአንዲት ሚስት ባል፣ ልጆቹም አማኞችና በመዳራት ወይም ባለመታዘዝ ስማቸው የማይነሣ ይሁን:: ⁷ኤጲስ ቆጶስ የእግዚአብሔር ሥራ ባለ ዐደራ እንደ መሆኑ የማይነቀፍ ሊሆን ይገባል፤ ይኸውም ትምክሕተኛ፣ ግልፍተኛ፣ ሰካራም፣ ጨቅጫቃና ተገቢ ባልሆነ መንገድ ለጥቅም የሚሮጥ ሊሆን አይገባም:: ⁸ከዚህ ይልቅ እንግዳ ተቀባይ፣ በጎ የሆነውን ነገር የሚወድ፣ ራሱን የሚገዛ፣ ቅን፣ ቅዱስና ጠንቃቃ ሊሆን ይገባል:: ⁹ሌሎችን ትክክል በሆነው ትምህርት እንዲያበረታታና ይህንኑ ትምህርት የሚቃወሙትን ይወቅስ ዘንድ እንደ ተማረው በታመነ ቃል የሚጸና መሆን አለበት::

¹⁰ዐመፀኞች፣ ለፍላፊዎችና አታላዮች የሆኑ ብዙ ሰዎች አሉና፤ በተለይም እነዚህ ከተገረዙት ወገን ናቸው:: ¹¹እነዚህን ዝም ማሰኘት ተገቢ ነው፤ ምክንያቱም ትክክል ባልሆነ መንገድ ጥቅም ለማግኘት ሲሉ ማስተማር የማይገባቸውን ነገር በማስተማር ቤተ ሰብን ሁሉ በመበከል ላይ ናቸውና:: ¹²ከራሳቸው ነቢያት አንዱ ስለ እነርሱ ሲናገር፣ "የቀርጤስ ሰዎች ዘወትር ውሸታሞች፣

1፥1 ሮሜ1፥1፤1ቆሮ 1፥1፤1ጢ ሞ2፥2:4፤ያዕ1፥1
1፥2 ዘኍ23፥19፤ 2ጢሞ1፥1:9፤ ቲቶ 3፥7፤ዕብ6፥18
1፥3ሉቃ1፥47፤2ቆሮ 1፥1:1ሞ1፥11፤2፥6፤ 6፥15፤2ጢሞ1፥10
1፥4 ሮሜ1፥7፤2ቆሮ 2፥13፤1ጢሞ1፥2
1፥5 ሐሥ11፥30፤ 27፥7
1፥6 1ተሰ3፥13፤ 1ጢሞ3፥2
1፥7 1ቆሮ4፥1፤1ጢ ሞ3፥1:3:8
1፥8 ሮሜ12፥13፤ 2ጢሞ3፥3፤ቲቶ2፥2: 5:6:12
1፥9 1ቆሮ16፥13፤ 1ጢሞ1፥10:19፤ 2ጢሞ1፥13፤3፥14
1፥10 ሐሥ10፥45፤ 11፥2፤ 1ጢሞ1፥6
1፥11 1ጢሞ5፥13
1፥12 ሐሥ2፥11፤ 17፥28

1፥1 *እምነትና … ዕውቀት፤* ጳውሎስ የእግዚአብሔር ባሪያና የክርስቶስ ሐዋሪያ ሆኖ የመሾሙ ጉዳይ፣ በቍጥር 2 ላይ ሰፋ ባለ ሁኔታ ተብራርቶአል (ሐሥ9፥15፤22፥15፤26፥16-18):: *የእግዚአብሔር ባሪያና፤* ጳውሎስ በዚህ ስፍራ ላይ ብቻ ራሱን፣ "የእግዚአብሔር ባሪያ" ብሎ ይጠራል፤ በሌላ ቦታ ግን ራሱን፣ "የክርስቶስ ባሪያ" ብሎ ነው የሚጠራው (ሮሜ1፥1፤ ገላ1፥10፤ ፊል1፥1):: ያዕቆብ ግን ራሱን የእግዚአብሔርና የክርስቶስ ባሪያ ብሎ ይጠራል (ያዕ1፥1):: *ባሪያና፤* የሮሜ1፥1 ማብ ይመ:: *ሐዋርያ፤* ልዩ በሆነ ሁኔታ በክርስቶስ የተሾመ ማለት ነው (የማር 6፥30፤1ቆሮ1፥1 ዕብ3፥1 ማብ ይመ)::

1፥2 *ተስፋ፤* የቈላ 1፥5 ማብ ይመ:: *የማይዋሸው፤* ከቀርጤስ ሰዎች ጋር (ቍ 12)እና ከዲያብሎስ ጋር (ዮሐ8፥44) በማነጻጸር ነው::

1፥3 *በወሰነውም ጊዜ፤* በእግዚአብሔር ዕቅድ ውስጥ የሆኑ ነገሮች፣ እርሱ እንዳቀደው ጊዜያቸውን ጠብቀው በታሪክ ውስጥ ይፈጽማሉ (1ጢሞ2፥6፤ 6፥15):: *በአዳኛችን በእግዚአብሔር፤* በዚህ መልእክት ውስጥ እግዚአብሔር አብ ሦስት ጊዜ፣ "አዳኝ" ተብሎአል (በዚህ ስፍራ፤ እንዲሁም 2፥10 እና 3፥4 ላይ ነው፤ እንዲሁም 1ጢሞ1፥1፤2፥3፤4፥10 ይመ):: ኢየሱስም ሦስት ጊዜ፣ "አዳኝ" ተብሎአል (ቍ4፤2፥13፤3፥6፤ እንዲሁም 2ጢሞ1፥10 ይመ):: *ቃሉን፤* ክርስቶስን ማዕከል ያደረገውን ሥልጣናዊ ቃል ማለት ነው::

1፥4 *የጋራችን በሆነው…እምነት፤* እውነተኛ አማኞች ሁሉ የሚጋሩትን ትክክለኛ እምነት ማለት ነው:: *እውነተኛ…ልጄ፤* እንደ ጢሞቴዎስ ሁሉ (1ጢሞ 1፥2)፣ ቲቶም በጳውሎስ አገልግሎት በክርስቶስ ያመነ መንፈሳዊ ልጁ ነው፤ ጳውሎስ አናሲሞስንም ልጄ ብሎ ጠርቶታል (ፊሞ 10):: *እውነተኛ፤* ሐሰት ያልሆነ ማለት ነው:: *ከአዳኛችንም፤* በሌሎቹ የጳውሎስ ሰላምታዎች ኢየሱስ፣ "ጌታ" ተብሎ ተጠርቶአል:: ጳውሎስ በመልእክታቱ ሁሉ፣ "አዳኝ" የሚለውን ቃል 12 ጊዜ የተጠቀመበት ሲሆን ከእነዚህ ውስጥ ግማሽ ያህሉ የሚገኙት በቲቶ መልእክት ነው::

1፥5 *በቀርጤስ የተውሁህ፤* ምንም እንኳ ይህ ነገር በሐዋርያት ሥራ ላይ ያልተጠቀሰ ቢሆንም፣ ጳውሎስና ቲቶ በቀርጤስ እንደ ነበሩ ያመለክታል:: ጳውሎስ ወደ ሮም በተጓዘበት ወቅት ለጥቂት ጊዜ ቀርጤስን ጐብኝቶአል (ሐሥ 27፥7-8)፤ አሁን ግን ከመጀመሪያው የሮም እስራቱ ተፈትቶ ወደ ፈቀደበት ስፍራ ለመሄድ ነጻነት አግኝቶአል (3፥12 ይመ):: *ሽማግሌዎችን እንድትሾም፤* ምናልባት ጳውሎስና ቲቶ በቀርጤስ ወንጌልን ሰብከው እንኳ ቢሆን፣ ቤተ ክርስቲያናትን ለማደራጀት በቂ ጊዜ ስላላገኙ ሊሆን ይችላል:: ሽማግሌዎችን መሾም የጳውሎስ የተለመደ ተግባሩ ነበር (ሐሥ14፥23)::

*1፥6-9፤* 1ጢሞ 3፥1-7 ከዚህ ክፍል ጋር ተመሳሳይ የሆነ የሽማግሌዎችን መመዘኛ ይሰጠናል፤ ነገር ግን መስፈርቶቹ ጢሞቴዎስና ቲቶ በሚያገለግሉባቸው የተለያዩ ሁኔታዎች ውስጥ የተሰጡ ናቸው:: "የሽማግሌዎችና የዲያቆናት መመዘኛ" የሚለውን ከጢሞቴዎስ አንደኛ ይመ::

1፥6 *የአንዲት ሚስት ባል፤* በመሠረቱ ሽማግሌዎች በማኅበረ ምእመናኑ መካከል ካሉት አረጋውያን የሚመረጡ ቢሆኑም እንኳ፣ ሰዎቹ ያገቡና ልጅ ያላቸው ሊሆኑ እንደሚገባቸው ጳውሎስ ተገንዝቦአል፤ ብቁ ሆኖ ከተገኘ ያላገባ ሰው ሽማግሌ አይሁን ማለት ግን አይደለም፤ ምናልባት መመዘኛው ሚስቱ የሞተችበት ሽማግሌ እንዲያገባ ይፈቅድለት ይሆናል (ከሮሜ7፥2-3፤1ቆሮ 7፥39፤1ጢሞ 5፥14 ጋር ያነጻጽሩ):: መሠረታዊው ሐሳቡ ለትዳሩ ታማኝ የሆነ ሰው የአንዲት ሚስት ባል ነው (የ1ጢሞ 3፥2 ማብ )::

1፥7 *ኤጲስ ቆጶስ፤* "ሽማግሌ" (ቍ5)፣ "ኤጲስ ቆጶስ" (ወይም "ጳጳስ") (ቍ7) የሚሉት ቃላት በተለዋዋጭነት ጥቅም ላይ ውለዋል (ከሐሥ20፥17:28፤ 1ጴጥ5፥1-2 ያነጻጽሩ):: "ሽማግሌ" የሚለው ቃል ብቃትን፣ ብስለትንና ልምድን ሲያሳይ፣ "ኤጲስቆጶስ" ወይም፣ "ጳጳስ" የሚሉት ቃላት ደግሞ የእግዚአብሔርን ሕዝብ የመምራትን ኀላፊነት የሚያሳዩ ናቸው::

1፥8 *ራሱን የሚገዛ፤* በቀርጤስ ከተማ እጅግ በጣም የሚያስፈልግ ነገር ነው (ቍ 10-14 ይመ)፤ ጳውሎስ ይህን ቃል በመጀመሪያውና በሁለተኛው ምዕራፎች ውስጥ ብቻ አምስት ጊዜ ተጠቅሞበታል (2፥2:5-6:12):: *ጠንቃቃ፤* ፍላጎትንና ምግባርን የመቈጣጠር ውስጣዊ ጥንካሬ ነው::

1፥9 *ትክክል በሆነው ትምህርት፤* ከሐዋርያት ትምህርት ጋር የሚጣጣመውን ትክክለኛ ትምህርት ማለት ነው (1ጢሞ 1፥10፤ 6፥3፤ 2ጢሞ 1፥13፤ 4፥3 ይመ):: ትምህርቱ፣ "ትክክል" የተባለበት ምክንያት በእምነት የሚያሳድግ በመሆኑ ብቻ ሳይሆን፣ ከመናፍቃን ሐሰተኛ ትምህርትም ስለሚጠብቅ ነው:: መልእክታተ ምጋቤ (1ኛና 2ኛ ጢሞቴዎስና ቲቶ) በአስተምህሮ፣ በእምነትና በንግግር ጤናማ (ትክክለኛ) መሆን የትምህርታቸው ማእከል ነው:: ስምንት ጊዜ የተጠቀሰውን "ትክክለኛ" የሚለውን ቃል የምናገኘው በሌሎች የጳውሎስ መልእክታት ውስጥ ሳይሆን በእነዚህ መልእክታት ውስጥ ነው::

*1፥10 ዐመፀኞች፤* ያመፁት በእግዚአብሔር ቃል ላይና እግዚአብሔር በሾማቸው አገልጋዮቹ በጳውሎስና በቲቶ ላይ ነው:: *ለፍላፊዎችና፤* ጳውሎስ እንዲህ ዐይነት ሰዎች ለመኖራቸው ለጢሞቴዎስም ጽፎለታል (1ጢሞ 1፥6):: *ብዙ ሰዎች፤* እነዚህ ችግር ፈጣሪዎች ሦስት ልዩ ባሕርያት አሏቸው፤ (1) እነዚህም በገላ 2፥12 ላይ እንዳሉት፣ "ከተገረዙት ወገን" እንደሚባሉት ናቸው፤ እነርሱም ለድነትም ሆነ ለቅድስና ወይም ለሁለቱም፣ መገረዝና የአይሁድን ወግ መጠበቅ አስፈላጊ ነው ብለው የሚያምኑ ናቸው (የገላትያን መግቢያ ይመ):: (2) ከመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት ውጭ የሆኑ የአይሁድን ተረታ ተረቶች እና የዘር ሐረግን መቍጠር ቁም ነገር አድርገው ይዘውታል (3፥9፤ 1ጢሞ 1፥4 እና በዚያ ያለውን ማብ ይመ):: (3) እግዚአብሔር መልካም ናቸው ካላቸው ነገሮች ራሳቸውን በማግለል የብሕትውናን ሕይወት ይኖራሉ (ቍ14-15)::

*1፥12፤* ይህ ጥቅስ በቀርጤስ ሰዎች ዘንድ ከፍተኛ ክብር

ክፉ አውሬዎችና ሰነፍ ሆዳሞች ናቸው” ብሎአል:: [13]ይህ ምስክርነት እውነት ነው፤ ስለዚህ አጥብቀህ ገሥጻቸው፤ ይኸውም ትክክለኛ እምነት እንዲኖራቸውና [14]የአይሁድን ተረት ወይም ከእውነት የራቁትን ሰዎች ትእዛዝ እንዳያዳምጡ ነው:: [15]ለንጹሓን ሁሉም ነገር ንጹሕ ነው፤ ለርኩሳንና ለማያምኑ ግን ንጹሕ የሆነ ምንም ነገር የለም፤ እንዲያውም አእምሮአቸውና ኅሊናቸው የረከሰ ነው:: [16]እግዚአብሔርን እናውቃለን ይላሉ፤ ዳሩ ግን በተግባራቸው ይክዱታል፤ አስጸያፊዎች፣ የማይታዘዙና ለበጎ ሥራ የማይበቁ ናቸው::

**2** አንተ ግን ከትክክለኛው ትምህርት ጋር ተስማሚ የሆነውን አስተምር:: [2]አረጋውያን ጭምቶች፣ የተከበሩ፣ ራሳቸውን የሚገዙና በእምነት፣ በፍቅርና በትዕግሥት ጤናማነት ያላቸው እንዲሆኑ ምከራቸው::

[3]እንዲሁም አሮጊቶች በአኗኗራቸው የተከበሩ እንዲሆኑ፣ በጎ የሆነውን የሚያስተምሩ እንጂ የሰው ስም የሚያጠፉ ወይም በወይን ጠጅ ሱስ የተጠመዱ እንዳይሆኑ አስተምራቸው፤ [4]እንዲህ ከሆኑ፣ ወጣት ሴቶች ባሎቻቸውንና ልጆቻቸውን እንዲወዱ ማስተማር ይችላሉ፤ [5]የእግዚአብሔር ቃል በማንም ዘንድ እንዳይሰደብ ራሳቸውን የሚገዙና ንጹሓን፣ በቤት ውስጥ በሥራ የተጠመዱ፣ ቸሮች፣ ለባሎቻቸው የሚገዙ እንዲሆኑ ያስተምሯቸው::

[6]እንዲሁም ወጣት ወንዶች ራሳቸውን እንዲገዙ ምከራቸው:: [7]በማንኛውም ነገር መልካም የሆነውን ነገር በማድረግ ራስህን አርአያ አድርገህ አቅርብላቸው:: በምታስተምራቸውም ትምህርት ጭምተኛነትን፣ ቁም ነገረኛነትን፣ [8]የማይነቀፍ ጤናማ አነጋገር አሳይ፤ ይኸውም ተቃዋሚ ስለ እኛ የሚናገረውን መጥፎ ነገር በማጣት እንዲያፍር ነው::

[9]ባሮች ለጌቶቻቸው በማንኛውም ነገር እንዲገዙ፣ ደስ እንዲያሰኟቸው፣ የአጸፋ ቃል እንዳይመልሱላቸው አስተምር፤ [10]አይስረቁ፤ ይኸውም በሁሉም መንገድ የአዳኛችን የእግዚአብሔር ትምህርት ይወደድ ዘንድ ፍጹም ታማኝ መሆናቸውን እንዲያስመሰክሩ ነው::

[11]ድነት የሚገኝበት የእግዚአብሔር ጸጋ ለሰዎች ሁሉ ተገልጦአልና፤ [12]ይህም ጸጋ ከኀጢአት መኖርንና ዓለማዊ ምኞትን ክደን፣ በአሁኑ ዘመን ራሳችንን በመግዛትና በጽድቅ፣ በእውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወት እንድንኖር

1፥13 1ጢሞ5፥20፤ ቲቶ2፥2
1፥14 ቈላ2፥22፤ 1ጢሞ1፥4፤2ጢሞ4፥4
1፥15 መዝ18፥26፤ ማቴ15፥10:11፤ማር 14-19፤ሐሥ 10፥9-16:28፤ ሮሜ14፥14:23፤ቈላ 2፥20-22፤1ጢሞ 6፥5
1፥16 ኤር5፥2፤12፥2፤ ሆሴ8፥2:3፤1ዮሐ2፥4
2፥1 1ጢሞ1፥10
2፥2 ቍ5:6:12፤1ጢሞ 3፥2፤5፥1፤ቲቶ1፥1:8:13
2፥3 1ጢሞ3፥8:11
2፥4 1ጢሞ5፥2
2፥5 ቍ2:6:12፤ ኤፌ 5፥22፤1ጢሞ 5፥14፤ 6፥1፤ቲቶ1፥8፤ዕብ 4፥12
2፥6 ቍ2:5:12፤ 1ጢሞ5፥1፤ቲቶ1፥8
2፥7 ቍ14፤1ጢሞ 4፥12
2፥8 1ጴጥ2፥12
2፥9 ኤፌ6፥5
2፥10 ማቴ5፥16፤ ሉቃ1፥47
2፥11 ሮሜ3፥24፤1ጢሞ 2፥4፤2ጢሞ1፥10
2፥12 ቍ2:5:6፤ 2ጢሞ3፥12፤ቲቶ 1፥8፤3፥3

---

የነበረውና በስድስተኛው መቶ ዓ.ቅ.ክ. በቀርጤስ ደሴት የኖስስ ተወላጅ ከነበረው ከባለ ቅኔው ከኤፒሜኒደስ የተወሰደ ቅኔ ነው:: እርሱ አስቀድሞ በትንቢት መልክ ተናገራቸው የተባሉ ነገሮች ተፈጽመዋል እየተባለም ይነገርለታል:: ጳውሎስ በሌሎቹ መልእክቶቹ ላይ ስለጠቀሳቸው ስለ ሌሎቹ አረማዊ አባባሎች ሐሥ 17፥28፤ 1ቆሮ 15፥33 እና ማብ ይመ:: በግሪክ ሥነ ጽሑፍ ውስጥ፣ "ቀርጤሳዊ" የሚል ቃል ከተጻፈ ቀጣፊ ማለት ነው::

1፥14 *የአይሁድን ተረት፤* የቍ 10 ማብ ይመ::

1፥15 *ለንጹሓን ሁሉም ነገር ንጹሕ ነው፤* ስርየትን በሚያስገኝ በክርስቶስ ሞት ለነጹ ክርስቲያኖች፣ "እግዚአብሔር የፈጠረው ማንኛውም ነገር መልካም ነውና፤ በምስጋና ከተቀበሉትም የሚጣል ምንም ነገር የለም" 1ጢሞ 4፥4:: *ለርኩሳንና ለማያምኑ ግን፣ ንጹሕ የሆነ ምንም ነገር የለም፤* የማያምኑ፣ በተለይም በቅዱሳት መጻሕፍት ላይ ያልተመሠረተ እምነት ያላቸው ባሕታውያንና በአንዳንድ ምግቦች እንዲሁም በጋብቻና በመሳሰሉት ላይ ጥርጣሬ የሚያሳዩ ወገኖች (ከ1ጢሞ 4፥3፤ ቈላ 2፥21 ጋር ያነጻጽሩ)፣ የእግዚአብሔርን ፍጥረት ሁሉ በምስጋና በሚቀበሉ በእውነተኛ ክርስቲያኖች ነጻነት ደስ አይሰኙም:: እነርሱ ግን በዚህ ፈንታ፣ ንጹሕ አይደለም በሚሏቸው ሰው ሠራሽ ነገሮች ላይ እገዳ ያደርጋሉ (ማቴ15፥10-11:16-20፤ ማር7፥14-19፤ ሐሥ 10፥9-16፤ ሮሜ14፥20 ይመ):: የዚህ ጥቅስ ትምህርት ከብዙ የአዲስ ኪዳን ትምህርት ጋር የሚቃረን አይደለም:: *ኅሊናቸው፤* 1ጢሞ 4፥2-3 ይመ::

1፥16 *በተግባራቸው ይክዱታል፤* የሐሰት መምህራን በሚያሳዩት ግብረ ገብ ማንነታቸው ይንጸባረቃል::

2፥1 *አንተ፤* የቲቶን ሥራ ከተወገዘው የሐሰት መምህራን ትምህርት ጋር ያነጻጽራል (1፥10-16)::

*2፥2-10፤* ትክክለኛ የሆነ አስተምህሮ በየትኛውም ዕድሜ፣ ጾታና ደረጃ ያሉ ሰዎች ትክክለኛ ባሕርይ እንዲኖራቸው ይጠይቃል::

*2፥2* እንደ ሽማግሌዎች ሁሉ፣ የዕድሜ ባለ ጸጋ የሆኑ ሰዎች መልካም ምሳሌ ሊሆኑ ይገባል:: *ጭምቶች፤* እነዚህ የዕድሜ ባለ ጸጋዎች አብዛኞቹ የቀርጤስ ሰዎች፣ "ሰነፍ ሆዳሞች" (1፥12) እንደ ሆኑት ሳይሆን፣ አስተዋዮችና ኀላፊነት የሚሰማቸው ሊሆኑ ይገባል::

2፥3 *እንዲሁም፤* እንደ ወንዶች ሁሉ፣ ሴቶችም ተመሳሳይ የሆነ ሥነ ምግባራዊ ሕግጋትን መጠበቅ አለባቸው:: *ስም የሚያጠፉ፤* ወሬና ሐሜት በቀርጤስ ሴቶች ዘንድ የተለመደ ነበር::

2፥4 *ባሎቻቸውንና ... እንዲወዱ፤* ባሎች ሚስቶቻቸውን እንዲወዱ እንደ ተመከሩ ሁሉ (ኤፌ5፥25)፣ ሚስቶችም ባሎቻቸውን እንዲወዱ ተመክረዋል፤ ነገር ግን በሁለቱ ምንባባት "መውደድ" የሚለው ቃል በግሪኩ የተለያዩ ቃላት ናቸው::

2፥5 *የእግዚአብሔር ቃል በማንም ዘንድ እንዳይሰደብ፤* ይህ ሐረግ ከእነዚህ ሥነ ምግባራዊ ምክሮች በስተጀርባ ጳውሎስን በእጅጉ የሚያሳስበውን ጥልቅ የሆነን መንፈሳዊ ሐሳብ ያመለክታል:: ጭንቀቱም ክርስቲያናዊ አኗኗር ለወንጌል ሥርጭት ከፍተኛ አስተዋፅኦ ስላለው ነው (ቍ 8-10 ይመ)::

*2፥7-8፤* ምናልባት ቲቶ ወጣት ከመሆኑ የተነሣ በቀርጤስ ቤተ ክርስቲያናት ዘንድ የሚገባውን ክብር ገና አላገኘ ይሆናል:: ከአንድ መሪ የሚጠበቀው የአነጋገሩ መልካምነት ብቻ ሳይሆን የአኗኗሩም አርአያነት ነው (ያዕ 3፥1)::

2፥7 *መልካም፤* በዚህ መልእክት፣ "መልካም" የሚለው ቃል አጽንዖት የተደረገበት ነው (1፥16፤ 2፥7:14፤ 3፥1:8:14)::

*2፥9-10፤* በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ላሉ ለተወሰኑ ሰዎች የተሰጠ መመሪያ ነው:: በሮማውያን ኅብረተሰብ ዘንድ የባርነት ሥርዐት ሥር የሰደደበት ወቅት ነበር፤ ባሮችም ክርስትናና የተቀበሉት በአዎንታ ነበር፤ ስለዚህ ክርስትናን ለተቀበሉ ባሪያዎች መመሪያ መስጠቱ አስፈላጊም ተገቢም ነበር (የኤፌ 6፥5 ማብ ይመ)::

2፥9 *ለጌቶቻቸው፤* የግሪኩ ቃል አንድ የባሪያ አሳዳሪ (ጌታ) በባሮቹ ላይ ያለውን የፈላጭ ቈራጭነት ሥልጣን ያመለክታል:: የሮም ባሮች ምንም ዐይነት መብት አልነበራቸውም፤ ዕድላቸውም እንዳሻቸው በሚያደርጓቸው በጌቶቻቸው እጅ ላይ ነበር::

2፥10 *የእግዚአብሔር ትምህርት ይወደድ ዘንድ፤* አማኝ የሆኑ ባሮች ለጌቶቻቸው በፈቃደኝነት ታማኝነታቸውንና ታዛዥነታቸውን በማሳየት፣ ልዩና ጠንካራ በሆነ መንገድ ለወንጌል ምስክር መሆን ይችላሉ::

*2፥11-14፤* በአጭሩ ጸጋ በአማኞች ሕይወት የሚያስከትለው ውጤት ተገልጾአል፤ እውነተኛ መንፈሳዊ ሕይወትን መኖር የሚያስችል የእግዚአብሔር ጸጋ ወደ ቅድስና ኑሮ ይመራል:: ስለ ክርስቶስ የምንሰጠው ምስክርነት ተቀባይነት እንዲያገኝ በቅድስና ሕይወት መደገፍ እንዳለበት ጳውሎስ አበክሮ ገልጾአል (ቍ 1-2:4-5:10፤ 3፥8)::

2፥11 *የእግዚአብሔር ጸጋ፤* ገና ኀጢአተኞችና ጠላቶቹ ሳለን የማይገባንን የእግዚአብሔርን ፍቅር በክርስቶስ ገለጸልን (ሮሜ 5፥6-10)፤ በእኛ ሃይማኖታዊ ተግባር ወይም መልካም ሥነ ምግባር ሊገኝ የማይችለውን ድነት ሰጠን (3፥5፤ ኤፌ 2፥8-9 ይመ)፤ ድነታችንም በመልካም ሥራ መገለጽ እንዳለበት ይህ ጸጋ ያስተምረናል (የቍ 14 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ኤፌ 2፥10 ይመ):: *ተገልጦአልና፤* ትክክለኛ የሆነ ሕይወት ትክክለኛ በሆነ ትምህርት ላይ ይመሠረታል::

2፥12 *በአሁኑ ዘመን፤* የ2ቆሮ 4፥4 ማብ ይመ:: *ያስተምረናል፤* ያስተምረናል የሚለው ቃል መመሪያ መስጠት ከሚለው ሐሳብ

ያስተምረናል፤ 13ይህም የተባረከ ተስፋችን የሆነውን የታላቁን የአምላካችንንና የአዳኛ ችንን የኢየሱስ ክርስቶስን ክብር መገለጥ በመጠባበቅ ነው፤ 14እርሱም ከክፋት ሊቤዥን መልካም የሆነውን ለማድረግ የሚተጋውን የእርሱ የሆነውን ሕዝብ ለራሱ ያነጻ ዘንድ ራሱን ስለ እኛ ሰጥቶአል።

15እንግዲህ ልታስተምር የሚገባህ እነዚህን ነው፤ በሙሉ ሥልጣን ምክር፤ ገሥጽም፤ ማንም አይናቅህ።

## በጎ የሆነውን ማድረግ

3 ሰዎች ለገዦችና ለባለ ሥልጣናት እንዲገዙ፣ እንዲታዘዙና መልካም የሆነውን ሁሉ ለማድረግ ዝግጁ እንዲሆኑ አሳስባቸው። 2እንዲሁም በማንም ላይ ክፉ እንዳይናገሩ፣ ሰላማውያን እንዲሆኑ፣ ለሰዎችም ሁሉ ከልብ የመነጨ ትሕትና እንዲያሳዩ አስገንዝባቸው።

3ቀድም ሲል እኛ ራሳችን ማስተዋል የጐደለን፣ የማንታዘዝ፣ የተታለልን፣ ለተለያየ ምኞትና ምቾት ባሪያ ሆነን የተገዛን ነበርን፤ እየተጣላንና እርስ በርስ እየተጠላላን በክፋትና በምቀኝነት እንኖር ነበር። 4ነገር ግን የአዳኛችን የእግዚአብሔር ቸርነትና ፍቅር በተገለጠ ጊዜ፣ 5ስላደረግነው የጽድቅ ሥራ ሳይሆን፣ ከምሕረቱ የተነሣ አዳነን። ያዳነንም ዳግም ልደት በሆነው መታጠብና በመንፈስ ቅዱስ መታደስ ነው፤ 6ይህንም መንፈስ እግዚአብሔር በአዳኛችን በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል በእኛ ላይ አትረፍርፎ አፈ ሰሰው፤ 7ይኸውም በጸጋው ጸድቀን የዘላለም ሕይወት ተስፋ ይዘን ወራሾች እንድን ሆን ነው። 8ይህም የታመነ ቃል ነው። በእግዚአብሔር ያመኑቱ መልካሙን ነገር ለማድረግ ራሳቸውን አሳልፈው ይሰጡ ዘንድ እነዚህን ነገሮች አስረግጠህ እንድትናገር እፈልጋለሁ። ይህ መልካምና ለማንኛውም ሰው የሚጠቅም ነው።

9ነገር ግን ከንቱ ከሆነ ክርክርና ከትውልድ ሐረግ ቈጠራ፣ ከጭቅጭቅና ስለ ሕግ ከሚነሣ ጠብ ራቅ፤ ይህ ዋጋ ቢስና ከንቱ ነውና። 10መከፋፈል የሚያመጣን ሰው አንድ ጊዜ ምከረው፤ ለሁለተኛ ጊዜ አስጠንቅቀው፤ ከዚያ ካለፈ ከእርሱ ጋር አንዳች ነገር አይኑርህ። 11እንዲህ ዐይነቱ ሰው የሳተና ኀጢአተኛ ነው፤ ራሱንም እንደሚኰንን ዕወቅ።

## የመጨረሻ ምክር

12አርጢሞንን ወይም ቲኪቆስን ወደ አንተ እንደ ላክሁ እኔ ወዳለሁበት ወደ ኒቆጵልዮን ለመምጣት የተቻለህን ሁሉ አድርግ፤ ክረምቱን በዚያ ላሳልፍ ወስኛለሁ። 13ሕግ ዐዋቂውን ዜማስንና አጵሎስን በጕዟቸው ለመርዳት የተቻለህን ሁሉ አድርግ፤ የሚያስፈልጋቸውንም ሁሉ አሟላ

2፥13 1ቆሮ1፥7፤ 1ጢሞ6፥14፤2ጴጥ1፥1
2፥14 ቈላ7፥III፥ 19፥5፤ዘጸ4፥20፤14፥2፤መዝ135፥4፤ምሳ16፥7፤ሚል3፥17፤ማቴ 1፥21፤5፥16፤20፥28፤ 2ቆሮ8፥21፤ ኤፌ 2፥10፤ቲቶ3፥1፤8:14፤ ዕብ1፥3፤ 1ጴጥ2፥9:12:15፤3፥13፤1ዮሐ1፥7
3፥1 ሮሜ13፥1፤2ጢሞ2፥21፤ቲቶ2፥14፤ 1ጴጥ2፥13:14
3፥2 ኤፌ4፥31
3፥3 ኤፌ2፥2
3፥4 ሉቃ1፥47፤ ኤፌ2፥7፤ቲቶ2፥11
3፥5 ሐሥ22፥16፤ ሮሜ11፥14፤12፥2፤ ኤፌ2፥9፤1ጴጥ1፥3
3፥6 ሮሜ5፥5
3፥7 ማቴ25፥46፤ ሮሜ3፥24፤8፥17: 24፤ቲቶ1፥2
3፥8 1ጢሞ1፥15፤ ቲቶ2፥14
3፥9 2ጢሞ2፥14 :16፤ቲቶ1፥10-16
3፥10 ሮሜ16፥17
3፥12 ሐሥ20፥4፤ 2ጢሞ4፥9:21
3፥13 ሐሥ18፥24

የበለጠ ትርጒም ያለው ነው፤ አንድን ሕፃን ልጅ ለማሠልጠን የሚደረገውን ማለትም መመሪያ መስጠትን፣ ድጋፍ ማድረግን፣ ማረምንና ሥነ ሥርዐት ማስያዝን ያጠቃልላል።

2፥13 *የተባረከ ተስፋችን ... ክብር መገለጥ፤* የክርስቶስን ዳግም ምጽአት የሚያመለክት ነው (1ጢሞ 6፥14፤ 2ጢሞ 4፥1 ይመ፤ እንዲሁም የ2ጢሞ 4፥8 ማብ ይመ)። *የታላቁን የአምላካችንንና የአዳኛችንን የኢየሱስ ክርስቶስን፤* በግሪኩ ሰዋሰው፣ "ታላቁ አምላካችንና አዳኛችን" የሚሉት ቃላት ኢየሱስ ክርስቶስን ማመልከታቸው የክርስቶስን ፍጹም አምላክነት በግልጽ የሚያሳዩ ናቸው (ሮሜ 9፥5 ይመ)።

*2፥14፤* ድነት ከፍርድና ከበደል መቤዥትንና ሥነ ምግባራዊ ንጽሕናን የሚያመጣ ነው፤ እንዲሁም ለሌሎች ጠቃሚ የሆነን ሥራ እንድንሠራ የሚያግዝ ነው።

*2፥15፤* ይህ ለቲቶ የተሠጠውን ኀላፊነትና ሥልጣን በአጭሩ አጠቃሎ ያስቀምጣል። *እነዚህን፤* ይህም በምዕራፉ ውስጥ ያለውን ትምህርት በሙሉ ማለት ነው።

*3፥1-2፤* የአዲስ ኪዳን ትምህርት በግልጽነት ላይ የሚያተኵር ብቻ ሳይሆን፣ በተግባር ስለሚገለጥም ሕይወት አያሌ መመሪያዎችን ያካትታል። አማኞች ሁሉ የመንግሥተ ሰማይ ዜጎች ቢሆኑም (ፊል 3፥20)፣ ለምድራዊ መንግሥት በመገዛት (ሮሜ 13፥1-7፤1ጴጥ 2፥13-17) የማኅበረሰቡ መልካም አኗኗር እንዲጐለብት እገዛ ማድረግ አለባቸው።

3፥1 *ለገዦችና ለባለ ሥልጣናት፤* ቃሉ በተለያየ የሥልጣን እርከን ላይ ያሉትን የመንግሥት ባለ ሥልጣናትን የሚያመለክት ነው (ከኤፌ 3፥10፡ 6፥12 ጋር ያነጻጽሩ)። *መልካም፤* የ2፥7 ማብ ይመ።

3፥4 *የእግዚአብሔር ቸርነትና ፍቅር፤* እግዚአብሔር በኀጢአት የወደቀውን ሰው ሊያጠፋው ባለመፈለጉ፣ የማዳን ሥራ የሠራበትን ምክንያት የሚገልጽ ነው (ከ2፥11 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥5 *ከምሕረቱ የተነሣ አዳነን፤* ድነት በሰው ጥረትና በጎ ሥራ የሚገኝ ሳይሆን፣ በእግዚአብሔር ምሕረት ብቻ የሚመጣ ነው። *ዳግም ልደት በሆነው መታጠብና፤* ከሌሎች ነገሮች ጋር ጥምቀት የመዳን ምልክት ነው። ጥምቀት ለዳግም ልደት አስፈላጊ ነገር ነው ማለት አይደለም፤ ሁሉም የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ዳግም ልደት የመንፈስ ቅዱስ ሥራ ብቻ እንደሆነ ያስተምራሉ (ዮሐ 3፥5 ይመ)፤ ይህም ሥርዐትን በማካሄድ የሚመጣ ወይም የሚሰናከል ጕዳይ አይደለም። *በመንፈስ ቅዱስ መታደስ፤* ይህም ዳግም ልደትን የሚያመለክት ነው።

3፥8 *የታመነ ቃል ነው፤* ከቊ 4-7 ላይ የተጠቀሰውን መሠረታዊ ትምህርት ባጭሩ የሚገልጽ ነው። ይህ ቃል በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የሚገኘው በዚህ ቦታ ላይ ብቻ ሲሆን፣ በመልእክታተ ምጋቤ ውስጥ አራት ጊዜ ተጠቅሶአል (1ጢሞ 1፥15፤ 3፥1፤ 4፥9፤ 2ጢሞ 2፥11)፤ በሌሎቹ የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ላይ ግን አይገኝም። *መልካሙን፤* የ2፥7 ማብ ይመ።

3፥9 *ስለ ሕግ፤* በ1፥10-16 ላይ የተገለጠውን ሁኔታ ያመለክታል፤ በኤፌሶንም ከዚሁ ጋር ተመሳሳይ የሆነ ችግር ነበር (1ጢሞ 1፥3-7 ይመ)።

3፥10 *መከፋፈልን የሚያመጣ ሰውን፤* ለዚህ ሐረግ የተሰጠው የግሪክ ቃል፣ የጥንቷ ቤተ ክርስቲያን መሠረታዊውን የክርስትና አስተምህሮዎችን እያጣመሙ ለሚያስተምሩ ሰዎች ትጠቀምበት የነበረ ቃል ነው።

*3፥11፤* ከትዕቢት የተነሣ እርማት ያለመቀበል የውስጥ ጠማምነትን የሚያሳይ ነገር ነው።

3፥12 *ቲኪቆስን፤* ከጳውሎስ ጋር እንዲሁም ጳውሎስ ልኮት ብዙ ቦታ የሄደ የጳውሎስ ታማኝ የሥራ ባልደረባው ነው (ሐሥ 20፥4፤ ኤፌ 6፥21-22፤ ቈላ 4፥7-8፤ 2ጢሞ 4፥12)። *ኒቆጵልዮን፤* "የድል ከተማ" ማለት ነው፤ በዚህ ስም ብዙ ከተሞች ተጠርተዋል፤ እዚህ ላይ የተገለጸው ግን፣ በምዕራቡ የግሪክ ዳርቻ ላይ ያለችውን የኤፒረስ ከተማን ነው። *ክረምቱን በዚያ ላሳልፍ ወስኛለሁ፤* ይህ የሚያመለክተው ጳውሎስ ይህን ሲጽፍ ገና ወደዚያ እንዳልደረሰና በሮም ለሁለተኛ ጊዜ ከመታሰሩ በፊት ወደ ፈለገበት ቦታ እንደ ልቡ ይንቀሳቀስ እንደ ነበረ ነው።

3፥13 *ሕግ ዐዋቂውን ዜማስንና፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ ስሙ የተወሣው እዚህ ላይ ብቻ ነው። ይህ ሰው ከይሁዲነት ወደ ክርስትና የተመለሰ ከሆነ፣ "ሕግ ዐዋቂ" ሲል፣ ሰውየው የኦሪት ሊቅ ነበር ማለት ሲሆን፣ አሕዛብ ከሆነ ግን ሮማዊ ዳኛ ነበር ማለት ነው። *አጵሎስን፤* የእስክንድርያ ተወላጅ እንዲሁም እጅግ የታወቀ የጳውሎስ የሥራ ባልደረባ ነው (ሐሥ 18፥24-28፤ 19፥1፤ 1ቆሮ 1፥12፤ 3፥4-6:22፤ 16፥12)። ይህን መልእክት ከጳውሎስ ተቀብለው ያመጡት እነዚህ ሰዎች ሳይሆኑ አይቀርም።

ቸው:: [14]ከእኛ ወገን ለሆኑት ለዕለት የሚያስፈልጋቸውን እንዲያገኙና ኑሮአቸውም ፍሬ የሌለው እንዳይሆን ለመልካም ሥራ መትጋትን ይማሩ ዘንድ ይገባቸዋል::

3፥14 ቲቶ2፥14

3፥15 ቈላ4፥18፤ 1ጢሞ1፥2

[15]ከእኔ ጋር ያሉት ሁሉ ሰላምታ ያቀርቡላችኋል:: ከእምነት የተነሣ ለሚወዱን ሰላምታ አቅርቡልን::

ጸጋ ከሁላችሁ ጋር ይሁን::

3፥14 *ለመልካም፤ መግቢያውን ይመ::*

# የሐዋርያው ጳውሎስ መልእክት
# ወደ ፊልሞና

## መግቢያ

### ጸሐፊው፣ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ

ጳውሎስ ይህን አጭር መልእክት የጻፈው የቈላስይስን መልእክት በጻፈበት ጊዜ ነው (በ60 ዓ.ም.፤ ቈላስይስ መግቢያ ላይ፣ "ጸሐፊው፣ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ" የሚለውን ይመ)። ይህን መልእክት ወደ ቈላስይስ የላከው በአናሲሞስና በቲኪቆስ እጅ ነው። ጳውሎስ ሁለቱን መልእክቶች የጻፈው ኤፌሶን በነበረበት ጊዜ ነው የሚሉ ቢኖሩም (በፊልጵስዩስ መግቢያ ላይ፣ "ጸሐፊው፣ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ" የሚለውን ይመ)፣ በሮም እስር ቤት እያለ መጻፉ ግን ግልጽ ነው።

### ተደራሲው፣ ዳራውና ዐላማው

ጳውሎስ ይህን መልእክት የጻፈው፣ ከቈላስይስ ባሪያ አሳዳሪዎች አንዱ ለነበረውና ፊልሞና ለሚባል አማኝ ነው (ከቈላ4፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ የባሪያ ሥርዐት በአዲስ ኪዳን ምን እንደሚመስል የኤፌ6፥5 ማብ ይመ)። ከባሪያዎቹ አንዱ አናሲሞስ፣ ከጌታው ሳይሰርቅ አልቀረም (ከቍ18 ጋር ያነጻጽሩ) በዚሁ ምክንያት ከቤት ጠፍቶ የኰበለለ ይመስላል፤ በሮም ሕግ ይህ ዐይነት ወንጀል በሞት የሚያስቀጣ ነበር። አናሲሞስ ከጳውሎስ ጋር የመገናኘት ዕድል በማግኘቱ በእርሱ አገልግሎት ክርስቲያን ሆነ (ቍ10 ይመ)። ከዚህም የተነሣ አናሲሞስ ወደ ጌታው ሊመለስ ፈቃደኛ በመሆኑ እንደ ክርስቲያን ወንድም እንዲቀበለው ጳውሎስ ይህን የግል መልእክት በመጻፍ ፊልሞናን ይማጠነዋል (ቍ16 ይመ)።

### አቀራረቡና ውቅሩ

አናሲሞስን ለመቀበል ፊልሞና ፈቃደኛ እንዲሆን ጳውሎስ በጥበብና በትሕትና መልእክቱን አለዝቦ ጽፎለታል (የቍ11 ማብ ይመ)። ለፊልሞና ያቀረበውን ልመና (ቍ4-21)፣ ጳውሎስ የጻፈው፣ የጥንት ግሪክና የሮም መምህራን ይህን ዐይነት ጽሑፍ የሚያዘጋጁበትን ዘዴ በመከተል ነው። ይህም የፍቅር ግኑኙነትን ለመመሥረት (4-10)፣ አስተሳሰብን ለመቀየርና (11-19) አንድን ሰው ለማሳመን (20-21) የሚጽፉበትን ዘዴ በመጠቀም ነበር። አናሲሞስ የሚለውን ስም የጠቀሰው፣ በእርሱና በፊልሞና መካከል ያለውን ፍቅርና ቅርርብ ከገለጠ በኋላ ሲሆን (ቍ10) ልመናውንም ያቀረበው በመልእክቱ መጨረሻ አካባቢ (ቍ17) ነው።

### አስተዋፅኦ

1. ሰላምታ (1-3)
2. ምስጋናና ጸሎት (4-7)
3. ጳውሎስ ስለ አናሲሞስ ያቀረበው ልመና (8-21)
4. የመጨረሻ ጥያቄ፣ ሰላምታና ቡራኬ (22-25)

**1** የክርስቶስ ኢየሱስ እስረኛ ከሆነ ጳውሎስና ከወንድማችን ከጢሞቴዎስ፤

ለውድ ወዳጃችንና አብሮን ለሚሠራው ለፊልሞና፣ [2]ለእኅታችን ለአፍብያ፣ አብሮን ወታደር ለሆነው ለአርክጳና በቤትህም ሳለ ችው ቤተ ክርስቲያን፤

[3]ከእግዚአብሔር ከአባታችን፣ ከጌታም ከኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋና ሰላም ለእናንተ ይሁን::

[4]አንተን በጸሎቴ በማስብህ ጊዜ ዘወትር አምላኬን አመሰግናለሁ፤ [5]ምክንያቱም በጌታ በኢየሱስ ያለህን እምነትና ለቅዱሳንም ሁሉ ያለህን ፍቅር ሰምቻለሁ:: [6]በክርስቶስ ስላለን መልካም ነገር ሁሉ በሚገባ ትረዳ ዘንድ፣ እምነትህን ለሌሎች በማካፈል እንድትተጋ እጸልያለሁ:: [7]ወንድሜ ሆይ፤ የቅዱሳንን ልብ ስላሳረፍህ ከፍቅርህ ታላቅ ደስታና መጽናናት አግኝቻለሁ::

[8]ስለዚህ ማድረግ የሚገባህን እንድታደርግ አዝህ ዘንድ በክርስቶስ ድፍረት ቢኖረኝም [9]በፍቅር እለምንሃለሁ፤ እንግዲህ ሽማግሌና አሁን ደግሞ የክርስቶስ ኢየሱስ እስረኛ የሆንሁት እኔ ጳውሎስ፣ [10]በእስር እያለሁ ስለ ወለድሁት ልጄ ስለ አናሲሞስ[ህ] እለ ምንሃለሁ:: [11]አስቀድሞ የሚጠቅምህ አልነ በረም፤ አሁን ግን ለአንተም ሆነ ለእኔ የሚጠቅም ሰው ሆኖአል::

[12]የልቤ ሰው የሆነውን እርሱን መልሼ ወደ አንተ ልኬዋለሁ:: [13]ስለ ወንጌል በታሰርሁበት ጊዜ በአንተ ፈንታ ሆኖ እንዲያገለግለኝ ለራሴ ላስቀረው ፈልጌ ነበር፤ [14]ነገር ግን አንተ የምታደርገውን መልካም ነገር ሁሉ በውዴታ እንጂ በግዴታ እንዳይሆን ሳላማክርህ ምንም ማድረግ አልፈልግም:: [15]ምናልባት ለጥቂት ጊዜ ከአንተ የተለየው፣ ተቀብለህ ለዘለቄታው አንተ ዘንድ እንድታቈየው ነው፤ [16]ከእንግዲህ ወዲህ ግን እንደ ባሪያ ሳይሆን ከባሪያ በላይ የሆነ ተወዳጅ ወንድም ነው:: ለእኔ ተወዳጅ ነው፤ ለአንተ ግን በሥጋም በጌታም እንዴት ይበልጥ ተወዳጅ ነው!::

[17]እንግዲህ እንደ ባልንጀራ ከቈጠርኸኝ እኔን እንደምትቀበለኝ አድርገህ ተቀበለው:: [18]አንተን የበደለህ ነገር ቢኖር ወይም የአንተ ብድር ቢኖርበት በእኔ ላይ ቍጠረው:: [19]እኔ ጳውሎስ ይህን በእጄ ጽፌልሃለሁ፤ ያለበትን እኔው እከፍልሃለሁ:: አንተም ራስህ የእኔ ስለ መሆንህ ምንም አልናገርም:: [20]ወንድሜ ሆይ፤ በጌታ እንድትጠቅመኝ እፈልጋለሁ፤ በክርስቶስ ልቤን አሳርፍልኝ:: [21]ታዛዥ መሆንህን በመተ ማመን፣ ከምጠይቀውም በላይ እንደምታደርግ በማወቅ እጽፍልሃለሁ::

[22]ከዚህም ሌላ፣ ጸሎታችሁ መልስ አግኝቶ ወደ እናንተ ለመምጣት ተስፋ ስለማደርግ ማረፊያ አዘጋጁልኝ::

[23]ከእኔ ጋር የክርስቶስ ኢየሱስ እስረኛ የሆነው ኤጳፍራ ሰላምታ ያቀርብልሃል፤ [24]እንዲሁም አብረውኝ የሚሠሩት ማርቆስ፣ አርስጥሮኮስ፣ ዴማስና ሉቃስ ሰላምታ ያቀርቡልሃል::

[25]የጌታ የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ከመንፈሳችሁ ጋር ይሁን::

1፥1 ቈላ9:23፤ሐሥ 16፥1፤2ቆሮ1፥1፤ኤፌ 3፥1፤ፊል2፥25
1፥2 ሮሜ16፥5፤ፊል 2፥25፤ቈላ4፥17
1፥3 ሮሜ1፥7
1፥4 ሮሜ1፥8:10
1፥5 ሐሥ20፥21፤ ቈላ1፥4፤1ተሰ3፥6
1፥7 ቈ 20፤ሮሜ 15፥32፤1ቆሮ16፥18፤ 2ቆሮ7፥4:13
1፥9 ቈ1:23፤1ቆሮ 1፥10፤ኤፌ3፥1
1፥10 ሐሥ21፥33፤ ቈላ4፥9፤1ተሰ2፥11
1፥13 ቈ10፤ሐሥ 21፥33
1፥14 2ቆሮ9፥7፤ 1ጴጥ5፥2
1፥16 ማቴ23፥8፤ ሐሥ1፥16፤1ቆሮ 7፥22፤1ጢሞ6፥2
1፥17 2ቆሮ8፥23
1፥18 ዘፍ43፥9
1፥19 1ቆሮ16፥21
1፥20 ቈ7፤1ቆሮ 16፥18
1፥21 2ቆሮ2፥3
1፥22 2ቆሮ1፥11፤ ፊል1፥19:25፤2፥24፤ ዕብ13፥19
1፥23 ቈ1፤ሮሜ 16፥7፤ቈላ1፥7፤4፥10
1፥24 ቈ1፤ሐሥ 12፥12፤19፥29፤ቈላ 4፥14፤2ጢሞ4፥10
1፥25 ገላ6፥18

[ህ]10 አናሲሞስ ማለት የሚጠቅም ማለት ነው

*1-2፤* ጳውሎስ ይህን መልእክት የጻፈው ለግለሰብ በመሆኑና መልእክቱም በጣም ግላዊ ስለሆነ፣ "እኛ" ወይም፣ "እናንተ" የሚለውን ሳይሆን "እኔ" የሚለውን ተውላጠ ስም ይጠ ቀማል:: ጳውሎስ "እኛ" እና "እናንተ" የሚሉትን ተውላጠ ስሞች የሚጠቀመው በቍጥር 22 እና 25 ላይ ብቻ ነው::

1 ***እስረኛ፤*** የኤፌ 3፥1 እና የፊል1፥13 ማብ ይመ:: ***ጢሞቴዎስ፤*** የቈላ1፥1 ማብ ይመ:: ***ፊልሞና፤*** በቈላስይስ ከተማ ወይም በአካባቢዋ ይኖር የነበረ ክርስቲያን እንዲሁም የአናሲሞስ አሳዳሪ ጌታ የነበረ ሰው ነው::

2 ***አፍብያ፤*** የፊልሞና ሚስት ልትሆን ትችላለች:: ***አርክጳ፤*** ቈላ4፥17 ይመ::

4 ***አንተን በጸሎቴ በማስብህ ጊዜ...አመሰግናለሁ፤*** የፊል1፥3-4 ማብ ይመ::

*5፤* ከቈላ1፥4 ጋር የሚነጻጸር ሲሆን፣ "በጌታ ኢየሱስ ያለህን እምነትና ለቅዱሳንም ሁሉ ስላለህ ፍቅር ሰምቻለሁ" የሚለው ዐረፍተ ነገር የግሪኩ አወቃቀር "ኪይዝም" በመባል የሚታወቀውን ሥነ ጽሑፋዊ ቅርጽ የተከተለ ነው:: "ኪይዝም" የሚለው ቃል የመጣው ካይ ከሚለው የግሪክ ፊደል ነው (X)::




7 ***ልብ፤*** የግሪኩ ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "አንጀት" የሚል ፍቺ አለው፤ በግሪኮች ምሳሌያዊ አነጋገር "አንጀት" የአዘኔታና የፍቅር መግለጫ ነው::

10 ***አናሲሞስ፤*** አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ከጌታው ከፊልሞና የኰበለለው አናሲሞስ ወደ ክርስትና የመጣው በሐዋርያው ጳውሎስ አማካይነት ነው (መግቢያውን ይመ):: ***ልጄ፤*** የ1ጢሞ 1፥2 ማብ ይመ::

11 ***የሚጠቅምህ አልነበረም...ጠቃሚ ሆኖአል፤*** በአናሲሞስ የስም ትርጕም ላይ የተደረገ ኀብር አገላለጽ ነው (የቍ10 ማብ ይመ)::

*11-19፤* ሉተር ይህን ክፍል፣ "ክርስቶስ በእግዚአብሔር አብ ዘንድ እንዳደረገልን ሁሉ ጳውሎስም በፊልሞና ዘንድ ለአናሲሞስ እንደዚሁ አድርጎለታል" ሲል ይገልጸዋል::

20 ***እንድትጠቅመኝ፤*** የዚሁ ቃል በግሪኩ ሲታይ በአናሲሞስ ስም ላይ የተደረገ ኀብር አገላለጽ ነው::

22 ***ከዚህም ሌላ፤*** በጥንት ደብዳቤ አጻጻፍ ከዋናው ርእሰ ጕዳይ በተጨማሪ ሌላ ነገር ማውሳት የተለመደ ነው:: እዚህም ላይ እንደምንመለከተው ብዙውን ጊዜ ተጨማሪው ነገር ጸሓፊውና ተቀባዩ እንዴትና መቼ መገናኘት እንደሚችሉ የሚያወሳ ነው::

23 ***ኤጳፍራ፤*** ቈላ 4፥12 ይመ::

24 ***ማርቆስ፤ አርስጥሮኮስ፤*** የቈላ 4፥10 ማብ ይመ:: ***ዴማስና ሉቃስ፤*** የቈላ 4፥14 ማብ ይመ::

# ወደ ዕብራውያን የተጻፈ መልእክት

### ጸሐፊው

የዚህ መልእክት ጸሐፊ፣ ማንነቱን አልገለጠም፤ ሆኖም ግን በመጀመሪያዎቹ የመልእክቱ ተደራሲያን ዘንድ የታወቀ ነው፤ መጽሐፉ ለ1200 ዓመታት ያህል (ከ400-1600 ዓ.ም.)፣ "በተለምዶ የጳውሎስ መልእክት ወደ ዕብራውያን" በመባል የሚታወቅ ቢሆንም በመጀመሪያዎቹ ምእተ ዓመ ታት ግን ተቀባይነት አላገኘም ነበር:: ከቤተ ክርስቲያን ዘመነ ተሐድሶ ወዲህ፣ ጳውሎስ የመልእክቱ ጸሐፊ እንዳልሆነ ይታሰባል:: የዕብራውያን መልእክትና የጳውሎስ መልእክቶች በሚያስተላልፉት ትምህርቶች መካከል አለመጣጣም አይታይም፤ ነገር ግን በልዩ ሁኔታ አጽንዖት በሚያደርጉባቸው ጉዳዮችና በአጻጻፍ ስልታቸው መካከል ከፍተኛ ልዩነት አለ:: ጳውሎስ በጻፋቸው መልእክቶች ውስጥ ስሙን ይገልጻል፤ የዕብራውያን መልእክት ጸሐፊ ጸታው ወንድ መሆኑን ከመግለጹ በስተቀር ማን እንደሆነ በየትም ስፍራ አላመለከተም (የ11፥32 ማብ ይመ):: በተጨማሪም፣ "ይህ ድነት በመጀመሪያ በጌታ ተነገረ፤ ከእርሱም የሰሙትም ለእኛ አረጋገጡ ልን::" (2፥3) የሚለው አረፍተ ነገር፣ ኢየሱስ በምድር ሲያገለግል የመልእክቱ ጸሐፊ ከእርሱ ጋር እንዳልነበረ፣ እንደ ጳውሎስም ከሞት ከተነሣው ጌታ ልዩ መገለጥን በቀጥታ እንዳልተቀበለ (ገላ1፥11-12) ያመለክታል የሚሉ አሉ::

የዕብራውያንን መልእክት ጸሐፊ በተመለከተ፣ የመጀመሪያው አስተያየት የተገኘው "20 ዲ ፑዲሲሺያ" (200 ዓ. ም.) በተባለው የጠርጡሊያኖስ ጽሑፍ ውስጥ ነበር፤ እርሱም በዚህ መጽሐፉ ውስጥ "በበርናባስ ስም ከተጻፈው፣ የዕብራውያን መልእክት" በማለት ጠቅሶ ጽፎአል:: የዕብራውያን መልእክት በሐዋርያት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሥልጣን ያለው፣ የብሉይ ኪዳን ሊቅ፣ እንዲሁም ዕብራዊ ክርስቲያን መሆኑን መልእክቱ ያስረዳል:: በርናባስም የተጠቀሱትን እነዚህን ሁኔታዎች የሚያሟላ ነበር፤ እርሱም አይሁዳዊ፣ ከካህናት ወገን የሆነ ሌዋዊ (ሐዋ4፥36) ነው:: ጳውሎስ ከተለወጠ በኋላም የእርሱ የቅርብ ጓደኛ ነበር:: የአንጾኪያ ቤተ ክርስቲያን በመንፈስ ቅዱስ መሪነት በርናባስንና ጳውሎስን ለወንጌል ሥራ ለይታ በመጀመሪያው የወንጌል ጉዞ ላከቻቸው (ሐሥ 13፥1-4):: የዕብራውያንን መልእክት ሳይጽፍ አይቀርም ተብሎ ትልቅ ግምት የሚሰጠው ሌላው ሰው ደግሞ፣ አጵሎስ ነው:: አጵሎስ የዚህ መልእክት ጸሐፊ እንደሆነ በመጀመሪያ የተነገረው በማርቲን ሉተር ሲሆን፣ ብዙ ምሁራንም ይደግፉታል:: አጵሎስ የእስክንድርያ ተወላጅ ሲሆን፣ በዕውቀቱና በንግግር ችሎታው፣ የታወቀ አይሁዳዊ ክርስቲያን ነበር:: የተማረና ቅዱሳት መጻሕፍትን ጠንቅቆ የሚያውቅ እንደነበርም ሉቃስ ጽፎአል (ሐሥ18፥24):: በቆሮንቶስ የወንጌል ሥራ ሲጀመር፣ አጵሎስ የጳውሎስ የሥራ ባልደረባ እንደነበረም እናውቃለን (1ቆሮ1፥12፤3፥4-6:22)::

### መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ

የዕብራውያን መልእክት የተጻፈው፣ የኢየሩሳሌም ከተማና ቤተመቅደሱ በ70 ዓ.ም. ከመደምሰሳቸው በፊት መሆን አለበት፤ ምክንያቱም:- (1) ከተጠቀሰው ዘመን በኋላ ተጽፎ ቢሆን ኖሮ፣ ጸሐፊው የቤተመቅደሱን መፍረስና የአይሁድን የመሥዋዕት ሥርዐት እንደ ቆመ በጠቀሰ ነበር (2) ጸሐፊው ስለቤተ መቅደሱና በቤተ መቅደሱ ውስጥ ይፈጸም ስለ ነበረው የካህናት አገልግሎት ሲናገር፣ በግሪክ ቋንቋ የቅርብ ጊዜን አመልካችን ተጠቅሞአል (5፥1-3፤7፥23:27፤8፥3-5፤9፥6-9:13:25፤10፥1:3-4:8:11፤13፥10-11 ይመ)::

### የመልእክቱ ተደራሲያን

መልእክቱ በመጀመሪያ የተጻፈው፣ ብሉይ ኪዳንን ጠንቅቀው ለሚያውቁ አይሁዳውያን ክርስቲያኖች ሲሆን፣ ይኸውም ወደ ይሁዲነት በመሳብ ላይ ለነበሩ ወይም ወንጌልን ከአይሁድ እምነት ጋር ለመቀላቀል (ከገላ 2፥14 ጋር ያነጻጽሩ) ይጥሩ ለነበሩ ምእመናን ነው:: እነዚህ አይሁዳውያን ክርስቲያኖች፣ በሙት ባሕር አጠገብ በሚገኘው ቁምራን በተባለ ስፍራ ከነበረው አንድ የአይሁድ ሃይማኖት ክፍል ጋር ለመደባለቅ ፍላጎት እንደነበራቸው የሚናገሩም አሉ:: እንዲሁም፣ የዚህ መልእክት ተቀባዮችን አስመልክቶ፣ ለእምነት ታዛዥ ከሆኑት አያሌ ካህናት መካከል የነበሩ ሰዎች (ሐሥ6፥7) ሊሆኑ እንደሚችሉ የሚናገሩም አሉ::

### የመልእክቱ መሪ ሐሳብ

የዕብራውያን መልእክት መሪ ሐሳብ፣ ኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔርን ጸጋ ለመግለጥና በእርሱም በኩል ይህ ጸጋ ወደ ሰው እንዲደርስ፣ ፍጹም ወደር የማይገኝለት ብቃት ያለው መሆኑን ለማሳየት ነው:: የመልእክቱ መግቢያ (1፥1-4)፣ ክርስቶስን እንከን የሌለበትና ከሁሉ የላቀ የእግዚአብሔር መገለጥ አድርጎ አቅርቦታል:: እርሱ ቀደም ሲል በብሉይ ኪዳን ተሰጥቶ ከነበረው መገለጥ ጋር ሲነጻጸር እጅግ የሚበልጥ ነው:: በብሉይ ኪዳን የተነገሩት ትንቢቶችና የተስፋ ቃሎች የተፈጸሙት ክርስቶስ መካከለኛ በሆነበት በአዲስ ኪዳን ነው:: ክርስቶስ፣ በብሉይ ኪዳን ከነበሩት ከነቢያት፣ ከመላእክት፣ የአሮጌው ኪዳን መካከለኛ ከነበረው ከሙሴ፣ ከአሮንና ከእርሱ

ዘር ከሆኑት ካህናት ሁሉ የላቀ መሆኑ በግልጽ ተጠቅሶአል:: በዚህ መልእክት ውስጥ “የተሻለ” እና “የላቀ” ለሚሉት ቃላት አቻ የሆኑ ሁለቱ የግሪክ ቃላት ዐሥራ አምስት ጊዜ ስለ ተጠቀሱ፣ መልእክቱ “የተሻለ ነገር መጽሐፍ” ተብሎ ሊጠራ ይችላል::

ይህ መሪ ሐሳብ፣ በአማኝ ሕይወት እንዴት ተግባራዊ ሊሆን እንደሚገባው በመጽሐፉ ውስጥ በስፋት ተገልጾአል:: አሮጌው የአይሁድ ሥርዐት፣ ልዩ በሆነ የክርስቶስ ክህነት ስለ ተተካ፣ ወደዚያ መመለስ ወይም በዚያ ሥርዐት መቀጠል፣ ከቶ ሊታሰብ እንደማይችል ለአንባቢው ተገልጾአል:: ከእንግዲህ የእግዚአብሔር ሕዝብ፣ እውነተኛ ወደ ሆነው ወደ ሰማያዊው የእግዚአብሔር መቅደስ፣ መግቢያ ስርየት ወዳገኘበት ወደ ኢየሱስ ሞት፣ ትንሣኤና ዕርገት ብቻ መመልከት ይኖርበታል:: አማኞች ወደኋላ እንዳያፈገፍጉ የሚታገላቸውን ፈተና በመቋቋም፣ የጀመሩትን መንፈሳዊ ውጊያ ጸንተው መቀጠል አለባቸው፤ አለበለዚያ፣ በምድረ በዳ የነበረው ዐመፀኛው የእስራኤል ሕዝብ የደረሰበት ዐይነት ቅጣት ሊደርስባቸው ይችላል::

**አስተዋፅኦ**

(1) መግቢያ:- የእግዚአብሔር አዲስ መገለጥ የበላይነት (1፥1-4)
(2) ክርስቶስ ከብሉይ ኪዳን መሪዎች የላቀ መሆኑ (1፥5-7፥28)
  ሀ. ክርስቶስ ከመላእክት የላቀ ነው(1፥5-2፥18)
    1. እንዴት እንደላቀም፣ የቅዱሳት መጻሕፍት ማስረጃ (1፥5-14)
    2. እግዚአብሔር በልጁ በኩል ራሱን መግለጡን ቸል እንዳይሉ የተሰጠ ምክር (2፥1-4)
    3. ከመላእክት እንደሚልቅ የቅዱሳት መጻሕፍት ተጨማሪ ማስረጃ (2፥5-18)
  ለ. ክርስቶስ ከሙሴ የላቀ ነው(3፥1-4፥13)
    1. ክርስቶስ እንዴት እንደላቀ ማስረጃ (3፥1-6)
    2. ወደ ድነት ዕረፍት ስለ መግባት የተሰጠ ምክር (3፥7-4፥13)
  ሐ. ክርስቶስ ከአሮናዊ ክህነት የላቀ ነው(4፥14-7፥28)
    1. በያዙት እምነት እንዲጸኑ የተሰጠ ምክር (4፥14-16)
    2. የካህን መመዘኛ (5፥1-10)
    3. ከመንፈሳዊ ድካም እንዲበረቱ የተሰጠ ምክር (5፥11-6፥12)
    4. የእግዚአብሔር ተስፋ እርግጠኛነት (6፥13-20)
    5. የክርስቶስ ክህነት የላቀ ስለመሆኑ (ም7)
(3) የሊቀ ካህናችን የላቀ የመሥዋዕትነት ሥራ (ም8-10)
  ሀ. የተሻለ ኪዳን (ም8)
  ለ. የተሻለ መቅደስ (9፥1-12)
  ሐ. የተሻለ መሥዋዕት (9፥13-10፥18)
  መ. ልዩ ልዩ ምክር (10፥19-39)
(4) በእምነት ስለ መጽናት የቀረበ የመጨረሻ ልመና (ም11-12)
  ሀ. የቀድሞ የእምነት አርበኞች ምሳሌነት (ም11)
  ለ. በእምነት ስለ መጽናት የተሠጠ ማበረታቻ (12፥1-11)
  ሐ. በእምነት ለመጽናት የተሠጠ ምክር (12፥12-17)
  መ. በእምነት ለመጽናት መነሣሣት (12፥18–29)
(5) ማጠቃለያ (ም13)
  ሀ. ስለ ክርስቲያናዊ ኑሮ የተሰጠ ተግባራዊ መመሪያ (13፥1-17)
  ለ. የጸሎት ጥያቄ (13፥18-19)
  ሐ. ቡራኬ (13፥20-21)
  መ. የግል አስተያየት (13፥22-23)
  ሠ. ሰላምታና የመጨረሻ ቡራኬ (13፥24-25)

## ልጁ ከመላእክት በላይ ነው

**1** እግዚአብሔር ከጥንት ጀምሮ በተለያየ ጊዜና በልዩ ልዩ መንገድ በነቢያት በኩል ለአባቶቻችን ተናግሮ፣ [2]በዚህ መጨረሻ ዘመን ግን ሁሉን ወራሽ ባደረገውና ዓለማትን በፈጠረበት በልጁ ለእኛ ተናገረን:: [3]እርሱ የእግዚአብሔር ክብር ነጸብራቅና የባሕርዩ ትክክለኛ ምሳሌ ሆኖ፣ በኀያል ቃሉ ሁሉን ደግፎ ይዞአል፤ የኀጢአት መንጻት ካስገኘ በኋላ በሰማያት በግርማው ቀኝ ተቀመጠ:: [4]ስለዚህ የወረሰው ስም ከመላእክት ስም እንደሚበልጥ ሁሉ፣ እርሱም ከመላእክት እጅግ የላቀ ሆኖአል::

[5]እግዚአብሔር፣
"አንተ ልጄ ነህ፤
እኔ ዛሬ ወልጄሃለሁ፤"[ሀ]

ወይስ ደግሞ፥
"እኔ አባት እሆነዋለሁ፤
እርሱም ልጅ ይሆነኛል" ያለው ከመላእክት ከቶ ለማን ነው?

[6]ደግሞም እግዚአብሔር በኵሩን ወደ ዓለም ሲያስገባ፣
"የእግዚአብሔር መላእክት ሁሉ[ለ] ይስገዱለት"
ይላል::

[7]ስለ መላእክትም ሲናገር፣
"መላእክቱን ነፋሳት፣
አገልጋዮቹንም የእሳት ነበልባል ያደርጋል"
ይላል::

[8]ስለ ልጁ ግን እንዲህ ይላል፤
"አምላክ ሆይ፤ ዙፋንህ ከዘላለም እስከ
ዘላለም ጸንቶ ይኖራል፤
ጽድቅም የመንግሥትህ በትር ይሆናል፤
[9]ጽድቅን ወደድህ፤ ዐመፃን ጠላህ፤
ስለዚህ እግዚአብሔር አምላክህ ከባልንጀ
ሮችህ በላይ አስቀመጠህ፣
የደስታንም ዘይት ቀባህ

[10]ደግሞም እንዲህ ይላል፤ "ጌታ ሆይ፤ አንተ
በመጀመሪያ የምድርን መሠረት አኖርህ፤

1፥1 ዘኍ12፥6:8፤ ሉቃ1፥70፤ዮሐ9፥29፤ ሐሥ2፥30፤ዕብ2፥2:3፤4፥8፤12፥25
1፥2 ቍ5፤ ዘዳ4፥30፤ መዝ2፥8፤ማቴ3፥17፤ 11፥27፤ 28፥18፤ ሐ1፥3፤ ዕብ3፥6:5፥8፤7፥28፤ 9፥26፤11፥3፤1ጴጥ1፥20
1፥3 ማር16፥19፤ ዮሐ1፥14፤14፥9፤ ቈላ1፥17፤ቲቶ2፥14፤ ዕብ7፥27፤9፥11-14
1፥4 ኤፌ1፥21፤ ፊል2፥9:10፤ዕብ8፥6
1፥5 2ሳሙ7፥14፤ መዝ2፥7፤ማቴ3፥17
1፥6 ዘዳ32፥43፤ መዝ97፥7፤ዮሐ3፥16፤ ቈ1፥18፤ዕብ10፥5
1፥7 መዝ104፥4
1፥8 ሉቃ1፥35
1፥9 ኢሳ61፥1:3፤ መዝ45፥6:7፤ፊል2፥9
1፥10 መዝ8፥6፤ ዘካ12፥1

[ሀ]5 ወይም እኔ ዛሬ አባት ሆንሁህ
[ለ]6 የሙት ባሕር ጥቅልሎችንና ሰብዓ ሊቃናትን ይመ

1፥1 *ከጥንት ጀምሮ*፤ ክርስቶስ ወደዚህ ዓለም ከመምጣቱ በፊት ያለውን ጊዜ የሚያመለክት ሲሆን፣ "በዚህ መጨረሻ ዘመን" (ቍ2) ከሚለው ጋር የሚነጻጸር ነው፤ የመሲሑ ዘመን የተጀመረውም ሰው ከሆነበት ጊዜ ጀምሮ ነው (የሐሥ 2፥17፤ 1ጢሞ4፥1፤1ዮሐ2፥18 ማብ ይመ::) *እግዚአብሔር ... ተናግሮ*፤ "ተናገረን" ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ (ቍ2):: የብሉይም ሆነ የአዲስ ኪዳን ምንጭ እግዚአብሔር ነው:: *ለአባቶቻችን* "ለእኛ" (ቍ2) ጋር ያነጻጽሩ:: *በነቢያት በኩል*፤ የብሉይ ኪዳን ጸሓፊዎች ሁሉ ምስክርነታቸው የመሲሑን መምጣት የሚያሳይ ስለ ነበር፣ እዚህ ላይ እንደ ነቢያት ተቈጥረዋል፤ "በልጁ" ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ (ቍ2)፤ ይህም ከነቢያት ጋር ሲነጻጸር በዐይነቱ አዲስና ልዩ የሆነ መገለጥ ነው:: *በተለያየ ጊዜና በልዩ ልዩ መንገድ*፤ የብሉይ ኪዳን መገለጥ ከፊል ማለትም ሙሉነትና ፍጹምነት የሚጐለው ነው::

*1፥2-3* በልጁ የመጣው መገለጥ የላቀ መሆኑን ለማሳየት ስለ ልጁ ሰባት ታላላቅ ነገሮች ተናግሮናል:: (1) *ሁሉን ወራሽ ባደረገውና*፤ ሥጋ የለበሰው ልጁ፣ የማዳን ሥራውን ከፈጸመ በኋላ የእግዚአብሔር በኵር ወራሽ ወደ ሚቀመጥበት ክብር ከፍ ከፍ አለ፤ ማለትም የእግዚአብሔር የሆነውን ሁሉ ርስት አድርጎ ተቀበለ ሮሜ 8፥17 ይመ:: (2) *ዓለማትን በፈጠረበት*፤ ዮሐ 1፥3፤ ቈላ 1፥16 ይመ:: (3)*የእግዚአብሔር ክብር ነጸብራቅና*፤ የፀሐይ ብርሃን ከራሷ ከፀሐይ ሊለይ እንደማይችል ሁሉ፣ የልጁም ነጸብራቅ እንዲሁ ከመለኮት ሊለይ አይችልም፤ ምክንያቱም እርሱ ራሱ አምላክና ከሥላሴ አካላት አንዱ ነው (ዮሐ 1፥14፤ 18):: (4)*የባሕርዩ ትክክለኛ ምሳሌ፤* ኢየሱስ የእግዚአብሔር አምሳል ወይም ነጸብራቅ ብቻ አይደለም፤ ልጁ ራሱ አምላክ ስለሆነ የእግዚአብሔር ህላዌ ትክክለኛ መልክ ነው:: (ከዮሐ 14፥9፤ ከቈላ 1፥15 ጋር ያነጻጽሩ):: (5) *ሁሉን ደግፎ ይዞአል፤* ክርስቶስ ዓለምን በትከሻው እንደተሸከመው እንደ ግሪኩ አምላክ እንደ አትላስ አይደለም:: ልጁ በእርሱ አማካይነት የተፈጠረውን ሁሉ (ቈላ 1፥17) በሥርዐት እንዲመራ አገጣጥሞ ይዞታል:: (6) *የኀጢአት መንጻት ካስገኘ በኋላ*፤ መንጻትን ያስገኘው በመስቀል ላይ በፈጸመው ቤዛነት ነው:: (7)*በሰማያት በግርማው ቀኝ ተቀመጠ*፤ በእግዚአብሔር ቀኝ መቀመጡ የቤዛነት ሥራው የተፈጸመ መሆኑንና ክርስቶስ አሁን ከእግዚአብሔር ጋር በሁሉ ላይ ጌታ ሆኖ እንደሚገዛ ያመለክታል (ቍ13፤8፥1፤10፥12፤12፥2፤ ኤፌ1፥20፤ ቈላ3፥1፤1ጴጥ3፥22 ይመ እንዲሁም የማር 16፥19 ማብ ይመ)::

1፥4 *ከመላእክት እጅግ የላቀ*፤ ለብዙ አይሁዳውያን መላእክት ከፍ ያሉ ፍጡራን ናቸው፤ አይሁድ ለመላእክት ከፍ ያለ ቦታ የሚሰጡት፣ የእግዚአብሔር ታላቅ መገለጥ አድርገው የሚቈጥሩት ሕግ በሲና ተራራ ላይ ሲሰጥ (የ2፥2 ማብ ይመ) መላእክትም በነገሩ ስለነበሩበት ነው:: የሙት ባሕር ጥቅልሎች እንደሚያመለክቱት፣ የመላእክት አለቃ የሆነው ሚካኤል በመሲሑ መንግሥት ትልቅ ስፍራ ይኖረዋል:: የዕብራውያን መልእክት ተደራሲዎች ከክርስቶስ (ከመሲሑ) ይልቅ ለመላእክት ከፍ ያለ ስፍራ ይሰጡ ወይም አይሰጡ የሚታወቅ ነገር የለም:: *ስም*፤ በአይሁድ ማኅበረ ሰብ ዘንድ ስም የአንድን ሰው ባሕርይና ተግባር የሚወክል ነው (የዘፍ 17፥5 ማብ ይመ):: ከዚህ ቀጥሉ ያለው ክፍል እንደሚያመለክተው ይህ ስም "ልጅ" የሚለው ነው፤ አንድም መልአክ ይህን ስም ለራሱ ሊጠቀም አይችልም::

*1፥5-14፤* ክርስቶስ ከመላእክት በላይ ነው የሚለው ጽኑ ሐሳብ፣ ከብሉይ ኪዳን በተወሰዱ ሰባት ጥቅሶች ተደግፎአል (መዝ2፥7፤2ሳሙ7፥14፤1ዜና17፥13፤ዘዳ32፥43፤መዝ104፥4፤ መዝ45፥6፤7መዝ102፥25-27፤መዝ110፥1 ይመ)፤ እነዚህም ጥቅሶች ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ፣ መላእክት የሚሰግዱለትና እንደ አብ እርሱም አምላክ ቢሆንም፣ ከአብ ግን የተለየ መሆኑን ያሳያሉ::

1፥5 *አንተ ልጄ ነህ፤ እኔ ዛሬ ወልጄሃለሁ፤* ይህ ጥቅስ (መዝ 2፥7) ክርስቶስ ከሙታን በተነሣ ጊዜ መፈጸሙን ለማሳየት በሐሥ 13፥33 ላይ ተጠቅሶአል (ከሮሜ 1፥4 ጋር ያነጻጽሩ):: *እኔ አባት እሆነዋለሁ፤ እርሱም ልጅ ይሆነኛል፤* አይሁድ 2ሳሙ 7፥14 (ይህ ጥቅስ የተወሰደው ከዚህ ክፍል ነው) እና መዝ 2 የሚመጣውን መሲሕ የሚያመለክቱ ናቸው ብለው ያምናሉ (ሉቃ 1፥32-33 ይመ):: ይህ ከዳዊት ቤት የሚወጣው ንጉሥ፣ መልአክ ወይም የመላእክት አለቃ አይደለም፤ ነገር ግን እርሱ የእግዚአብሔር ልጅ ነው::

1፥6 *በኵሩን*፤ የቈላ 1፥15 ማብ ይመ:: *የእግዚአብሔር መላእክት ሁሉ ይስገዱለት*፤ ይህ ጥቅስ የተወሰደው ከመዝ 97፥7 ሳይሆን አይቀርም:: በብሉይ ኪዳን ጌታ *እግዚአብሔርን* የሚያመለክተው ይህ ዐረፍተ ነገር እዚህ ላይ ክርስቶስን አመልክቷል:: ይህም ክርስቶስ ፍጹም አምላክ እንደሆነ በግልጽ ያሳያል:: ከክርስቶስ ጋር የተነጻጸሩት እነዚህ መላእክት ለእርሱ በመስገድ ልዕልናውን እንዲያውጁ ታዘዋል::

1፥7 *መላእክቱን ነፋሳት፣ አገልጋዮቹንም የእሳት ነበልባል ያደርጋል*፤ መዝ 104፥14፤ ኀይለኛው ነፋስና መብረቅ የእግዚብሔርን ፈቃድ የሚፈጽሙ መልእክተኞች እንደሆኑ ይናገራል:: የዕብራውያን መልእክት ጸሓፊ ጥቅሶቹን የወሰደው ተደራሲዎቹ በሚገባ ከሚያውቁት ከሰብዓ ሊቃናት ትርጕም (ከዕብራይስጥ ወደ ግሪክ ቋንቋ የተመለሰው) ሲሆን፣ በብሉይ ኪዳንና በአዲስ ኪዳን መካከል ባሉት ዘመናት ስለ መላእክት የሚሰጠው አስተምህሮ እያደገ እንደመጣ ያመለክታል::

1፥8 *ስለ ልጁ ግን እንዲህ ይላል፤ አምላክ ሆይ፤ ዙፋንህ ከዘላለም እስከ ዘላለም ጸንቶ ይኖራል፤* የመልእክቱ ጸሓፊ መሲሐዊው (ከዳዊት ወገን) የሆነው ንጉሥ አምላክ እንደሆነ የሚያሳዩ ክፍሎችን እየመረጠ ጠቅሷል፤ ይህም ልጁ ከመላእክት በላይ መሆኑን ይበልጥ የሚገልፅ ነው::

1፥10 *ጌታ ሆይ፤ አንተ በመጀመሪያ የምድርን መሠረት አኖርህ፤* በቍጥር 6 እንደ ተመለከተው ሁሉ እዚህም ላይ ያህዌን የሚያመለክተው "ጌታ ሆይ" የሚለው ሐረግ ለልጁ መጠሪያ ሆኖአል::

ስማያትም የእጆችህ ሥራ ናቸው::
[11]እነርሱ ይጠፋሉ፤ አንተ ግን ጸንተህ ትኖራለህ፤
ሁሉም እንደ ልብስ ያረጃሉ፤
[12]እንደ መጐናጸፊያ ትጠቀልላቸዋለህ፤
እንደ ልብስም ይለወጣሉ::
አንተ ግን ያው አንተ ነህ፤
ዘመንህም ፍጻሜ የለውም::"
[13]እግዚአብሔር፣
"ጠላቶችህን የእግርህ መረገጫ እስከማድረግ ልህ ድረስ፣
በቀኜ ተቀመጥ" ያለው ከመላእክት ከቶ ለማን ነው?

[14]መላእክት ሁሉ መዳንን የሚወርሱትን ለማገልገል የሚላኩ አገልጋይ መናፍስት አይደሉምን?

## ትኵረት የሚያስፈልጋቸው ነገሮች

**2** ስለዚህ ከሰማነው ነገር ስተን እንዳንወድቅ፣ ለሰማነው ነገር አብልጠን ልንጠነቀቅ ይገባናል:: [2]ምክንያቱም በመላእክት በኩል የተነገረው ቃል ጽኑ ከሆነና ማንኛውም መተላለፍና አለመታዘዝ ተገቢውን ቅጣት ከተቀበለ፣ [3]እኛስ እንዲህ ያለውን ታላቅ ድነት ቸል ብንል እንዴት ልናመልጥ እንችላለን? ይህ ድነት በመጀመሪያ በጌታ ተነገረ፤ ከእርሱ የሰሙትም ለእኛ አረጋገጡልን::

1፥11 ኢሳ34፥4፤ 51፥6፤ዕብ12፥27
1፥12 መዝ102፥25-27፤ ዕብ13፥8
1፥13 ቍ3፤ኢያ10፥24፤ መዝ110፥1፤ ማቴ22፥44፤ ማር16፥19፤ዕብ10፥13
1፥14 ዳን7፥10፤ መዝ91፥11፤103፥20፤ ማቴ25፥34፤ ማር10፥17፤ ሐሥ20፥32 ሮሜ11፥14፤ ዕብ2፥3፤5፥9፤9፥28
2፥1 ሮሜ11፥22
2፥2 ዘዳ33፥2፤ ሐሥ7፥53፤ገላ3፥19፤ ዕብ1፥1
2፥3 ሉቃ1፥2፤ ዕብ1፥2፤10፥29
2፥4 ማር16፥20፤ ዮሐ4፥48፤1ቆሮ12፥4፤ ኤፌ1፥5
2፥6 ኢዮ7፥17፤ መዝ144፥3፤ዕብ4፥4
2፥8 መዝ8፥4-6፤ ማቴ22፥44
2፥9 ቍ7፤ሐሥ3፥13፤ 2ቆሮ5፥15፤ፊል2፥7-9
2፥10 ሉቃ24፥26፤ ሮሜ11፥16፤ዕብ5፥8፡ 9፤7፥28

[4]እግዚአብሔርም በምልክት፣ በድንቅና በልዩ ልዩ ታምራት እንዲሁም እንደ ፈቃዱ በታደሉት የመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች ስለዚሁ ነገር መስክሮአል::

## ኢየሱስ ወንድሞቹን መሰለ

[5]ይህን የምንናገርለትን መጪውን ዓለም ለመላእክት አላስገዛም፤ [6]ነገር ግን አንዱ በሌላ ስፍራ እንዲህ ብሎ መስክሮአል፤
"ታስታውሰው ዘንድ ሰው ምንድን ነው?
ታስብለትስ ዘንድ የሰው ልጅ ምንድን ነው"
[7]ከመላእክት ጥቂት[a] አሳነስኸው፤
የክብርና የምስጋና ዘውድ ጫንህለት፤
[8]ሁሉንም ከእግሮቹ በታች አስገዛህለት::

እግዚአብሔር ሁሉን ከበታቹ ሲያስገዛለት፣ ያላስገዛለት ምንም ነገር የለም፤ ይሁን እንጂ በአሁኑ ጊዜ ሁሉም ነገር ተገዝቶለት አናይም:: [9]ነገር ግን በእግዚአብሔር ጸጋ ስለ ሰው ሁሉ ሞትን ይቀምስ ዘንድ ከመላእክት ጥቂት እንዲያንስ ተደርጎ የነበረው ኢየሱስ፣ የሞትን መከራ በመቀበሉ አሁን የክብርና የምስጋና ዘውድ ተጭኖለት እናየዋለን::

[10]ሁሉ ነገር ለእርሱና በእርሱ የሚኖር እግዚአብሔር፣ ብዙ ልጆችን ወደ ክብር ለማምጣት፣ የድነታቸውን መሥራች በመከራ ፍጹም ሊያደርገው የተገባ ነበር::

[a]7 ወይም ለጥቂት ጊዜ

1፥13 *በቀኜ ተቀመጥ*፤ የቍ 2-3 ማብ ይመ:: በዕብራውያን መልእክት ውስጥ መዝ 110 ከኢየሱስ ጋር ተያይዞ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶአል (ቍ3፥13፤5፥6፤10፤6፥20፤7፥3፤11፤17፤21፤8፥1፤10፥12-13፤ 12፥2)::

1፥14 *አገልጋይ መናፍስት*፤ ክርስቶስ ነግሦአል፣ መላእክት ግን ለማገልገል የሚላኩ ናቸው::

*2፥1-4*፤ በመልዕክቱ ውስጥ ቦልፍ ቦታ ከያዙት አምስት የማስጠንቀቂያ ክፍሎች መካከል የመጀመሪያው ነው (3፥7-4፥13፤5፥11-6፥12፤10፥19-39፤12፥14-29 ይመ)::

2፥1 *ከሰማነው ነገር*፤ ክርስቶስ አምላክና ሰው መሆኑን እንዲሁም በመስቀል ላይ የፈጸመውን ቤዛነት ጨምሮ የወንጌልን መልእክት የሚያሳይ ነው:: *እንዳንወድቅ*፤ በልጁ አማካይነት ከተሰጠው ታላቅ መገለጥ እንዳንጐድል ነው::

2፥2 *በመላእክት በኩል የተነገሬው ቃል*፤ በሲና ተራራ ላይ ለሙሴ የተሰጠው ሕግ ነው:: ሕጉ በተሰጠበት ጊዜ፣ መላእክት ንቁ ተሳትፎ አድርገው እንደ ነበር በዘዳ32፥2 ላይ ተጠቅሶአል:: "እልፍ አእላፍ" መዝ 68፥17፤የሐሥ7፥38፡ 53፤ገላ 3፥19::

2፥3 *እንዲህ ያለውን ታላቅ ድነት*፤ እዚህ ላይ የመከራከሪያው ነጥብ ከትንሹ ወደ ትልቁ የሚያመራ ሲሆን፣ ወንጌል ከሕግ በላይ ነው የሚለው ትልቅ ስፍራ ተሰጥቶታል:: በመሆኑም ሕጉን አለመታዘዝ ቅጣት የሚያመጣ ከሆነ፣ ወንጌሉን አለመታዘዝ ደግሞ የበለጠ ቅጣት ያመጣል:: *የሰሙትም ለእኛ አረጋገጡልን፤* የዐይን ምስክር የነበሩት ሐዋርያት (2ጴጥ 1፥16፤ 1ዮሐ 1፥1 ይመ)፣ በመጀመሪያ በክርስቶስ የተሰበከውን መልእክት አረጋግጠዋል::

2፥4 *በምልክት፣ በድንቅና በልዩ ልዩ ታምራት*፤ እግዚአብሔር የወንጌልን መልእክት ያጸና የነበረው ልዕለ ተፈጥሮአዊ ነገሮችን በመፈጸም ለምሳሌ በሽተኞችን በመፈወስ ነው (የሐሥ 3፥7-9፡11-12፡16ይመ) *የመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች፤* በልሳን መናገር፣ የመሳሰሉትን ነው (የሐሥ 2፥4-12 ይመ)፤ *እንደ ፈቃዱ በታደሉት*፤ 1ቆሮ 12፥4-11 ይመ::

*2፥5-18* የመዝ8፥4-6 ማብራሪያ ሲሆን፣ ክርስቶስ ከመላእክት በላይ መሆኑን ለማሳየት ጸሐፊው የጀመረውን ገለጻ የሚቀጥል ነው፤ ክርስቶስ የሰው ልጆች በምድር ላይ ገዢ በመሆን እንዲያከናውኑት የተሰጣቸውን ተግባር በመፈጸምና የወደቁትን መላእክት ሳይሆን በኀጢአት የወደቁ ሰዎችን በመዋጀት ለእነርሱ የተሰጠውን ተልእኮ ፈጸመ:: ይህን ሁሉ ለማድረግ ክርስቶስ ሰው መሆን ነበረበት (ቁ 11፤14 ይመ)::

2፥5 *መጪውን ዓለም ለመላእክት አላስገዛም*፤ አንዳንድ ሰዎች፣ የዚህ መልእክት ተደራሲዎች የሚመጣው ዓለም በመላእክት አገዛዝ ሥር ይውላል የሚለው አመለካከት ሳይማርካቸው አልቀረም ይላሉ (የ1፥4 ማብ ይመ):: ሌሎች ደግሞ ጸሐፊው የሚጥረው ተደራሲዎቹ ወደ ቀድሞው የይሁዲ እምነታቸው እንዳይመለሱ ነው ይላሉ:: ያም ሆነ ይህ የመልእክቱ ጸሐፊ፣ አዲሱን መገለጥ ያመጣው ክርስቶስ፣ በሲና ተራራ ላይ ሕግ ሲሰጥ ተሳትፎ ካደረጉት መላእክት እንደሚበልጥ በተጨባጭ አሳይቷል::

2፥6 (ሀ)፤*አንዱ በሌላ ስፍራ እንዲህ ብሎ መስክሮአል*፤ እንደ መዝ 8፥4-6 ያለ በሚገባ የሚታወቅ ጥቅስ ቦታው የት እንደሆነ ለይቶ ማመልከት አስፈላጊ አይደለም::

2፥6 (ለ)-8 መዝሙረኛው ዕፁብ ድንቅ በሆነው የፍጥረት ሥርዐትና ፍጥረተ ዓለም ውስጥ በሚታዩት ልዩ ልዩ የእግዚአብሔር እጅ ሥራዎች በመገረም፣ እንደ ኢምንት የሚቈጠረውን ሰው እግዚአብሔር በሌሎች ፍጥረታት ላይ ገዥ አድርጎ በመሾም፣ ያጐናጸፈውን ታላቅ ክብር እያሰበ ይደነቃል (ዘፍ 1፥26-28፤ እና ማብ ይመ)::

2፥7 *ከመላእክት*፤ የመዝ 8፥5 ማብ ይመ::

2፥8 *ሁሉንም*፤ እግዚአብሔር በመጀመሪያ የነበረው ዐላማ ሰው በሥነ ፍጥረት ላይ ገዥ እንዲሆንና ለእግዚአብሔር ብቻ እንዲገዛ ነው:: በኀጢአት ምክንያት ግን የእግዚአብሔር ዐላማ ሙሉ በሙሉ ገና እውን አልሆነም:: እንዲያውም ሰው ራሱ "በባርነት ውስጥ" ነው ያለው (ቍ 15)::

2፥9 *ኢየሱስ ...አሁን የክብር ዘውድ ተጭኖለት*፤ መዝ 8፣ እዚህ ላይ በተለይ ኢየሱስን ለማመልከት ገብቶአል:: ሰው በምድር ላይ ገዥ እንዲሆን ለተሰጠው አዲስ ኀላፊነት ቀዳሚ እንደ መሆኑ መጠን፣ ለአጭር ጊዜ ከመላእክት ቢያንስም አሁን ግን በእግዚአብሔር ቀኝ የክብርና የምስጋና ዘውድ ተጭኖለታል:: ፍጹም በሆነው ሕይወቱ፣ በመስቀል ሞት የተዋጀው ሰው በሚመጣው መንግሥት፣ በመዝ 8 ላይ የተነገረው ቃል እንዲፈጸምለት አድርጎአል:: ያን ጊዜ ሰው በሥነ ፍጥረት ላይ ይሠለጥናል::

2፥10 *ብዙ ልጆችን ወደ ክብር*፤ በክርስቶስ የሚያምኑ ሁሉ አንድ ልጁ በሆነው በክርስቶስ አማካይነት የእግዚአብሔር ልጆች ሆነዋል (ከዮሐ 1፥12-13 ጋር ያነጻጽሩ):: *መሥራች*፤ የግሪኩ ቃል በአዲስ ኪዳን ውስጥ የሚገኘው አራት ጊዜ ብቻ ነው፤ እዚህ ላይ፤ 12፥2፤ የሐሥ 3፥15፤5፥31፡ ("ራስ"):: *በመከራ ፍጹም ሊያደርገው*፤ ክርስቶስ በምግባሩም ሆነ በመንፈሱ ፍጹም

[11]ሰዎችን የሚቀድሰውና የሚቀደሱት ሰዎች ከአንድ ቤተ ሰብ ናቸው፤ ስለዚህ ኢየሱስ ወንድሞች ብሎ ሊጠራቸው ዐያፍርም፤ [12]እንዲህም ይላል፤

"ስምህን ለወንድሞቼ እነግራቸዋለሁ፤
በጉባኤም መካከል ምስጋናህን እዘምራለሁ።"

[13]እንዲሁም፣

"እኔ በእርሱ እታመናለሁ።"

ደግሞም እንዲህ ይላል፤

"እነሆ፤ እኔና እግዚአብሔር የሰጠኝ ልጆች።"

[14]ልጆቹ በሥጋና በደም እንደሚካፈሉ እርሱ ራሱ ደግሞ ያንኑ ተካፈለ፤ ይኸውም በሞት ላይ ኀይል ያለውን ዲያቢሎስን በሞቱ ኀይል እንዲደመስስ ነው፤ [15]እንዲሁም በሕይወት ዘመናቸው ሁሉ በሞት ፍርሀት ባርነት የታሰሩትን ነጻ እንዲያወጣ ነው። [16]እርሱ የመጣው መላእክትን ለመርዳት ሳይሆን፣ የአብርሃምን ዘር ለመርዳት እንደ ሆነ ግልጽ ነው። [17]ስለዚህ በሁሉም ነገር ወንድሞቹን መምሰል ተገባው፤ ይህንም ያደረገው መሐሪና ታማኝ ሊቀ ካህናት ሆኖ እግዚአብሔርን ለማገልገልና ለሕዝቡ የኀጢአትን ስረየት[m] ለማስገኘት ነው። [18]እርሱ ራሱ በተፈተነ ጊዜ መከራን ስለ ተቀበለ፣ የሚፈተኑትን ሊረዳቸው ይችላልና።

2፥11 ማቴ28፥10፤ ኤፌ5፥26፤ዕብ13፥12
2፥12 መዝ22፥22፤ 68፥26
2፥13 ኢሳ8፥17፡18፤ ዮሐ10፥29
2፥14 ዘፍ3፥15፤ ዮሐ1፥14፤1ቆሮ15፥50፡ 54-57፤ ኤፌ6፥12፤ 2ጢሞ1፥10፤1ዮሐ3፥8
2፥15 2ጢሞ1፥7
2፥16 ሉቃ3፥8
2፥17 ቍ14፤ ሮሜ3፥25፤ፊል2፥7፤ ዕብ3፥1፤4፥14፡15፤ 5፥1፡2፡5፡10፤7፥26፡ 28፤8፥1፡3፤9፥11
2፥18 ዕብ4፥15
3፥1 ሮሜ 8፥28፤2ቆሮ9፥13፤ 1ጢሞ6፥12፤ ዕብ2፥11፡17፤4፥14፤ 10፥23
3፥2 ቍ5፤ዘኍ12፥7
3፥3 ዘዳ34፥12
3፥4 ዘፍ1፥1
3፥5 ቍ2፤ዘፀ14፥31፤ ዘኍ12፥7

## ኢየሱስ ከሙሴ በላይ ነው

**3** እንግዲህ የሰማያዊው ጥሪ ተካፋዮች የሆናችሁ ቅዱሳን ወንድሞች ሆይ፤ የእምነታችን ሐዋርያና ሊቀ ካህናት የሆነውን ኢየሱስን አስቡ። [2]ሙሴ በእግዚአብሔር ቤት ሁሉ ላይ ታማኝ እንደ ነበር፣ እርሱም ለሾመው ታማኝ ነበር። [3]ቤትን የሚሠራ ከቤቱ ይልቅ የሚበልጥ ክብር እንዳለው፣ ኢየሱስም ከሙሴ የሚበልጥ ክብር የተገባው ሆኖ ተገኝቶአል፤ [4]እያንዳንዱ ቤት የራሱ ሠሪ አለው፤ ነገር ግን ሁሉን የሠራ እግዚአብሔር ነው። [5]ሙሴ ወደ ፊት ስለሚነገረው ነገር እየመሰከረ፣ በእግዚአብሔር ቤት ሁሉ ላይ እንደ አንድ ታማኝ አገልጋይ ነበር፤ [6]ክርስቶስ ግን በእግዚአብሔር ቤት ላይ እንደ ታማኝ ልጅ ነው። እኛም የምንተማመንበትንና የምንመካበትን ተስፋ አጥብቀን ብንይዝ ቤቱ ነን።

## ስለ አለማመን የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

[7]ስለዚህ መንፈስ ቅዱስ እንደሚል፣
"ዛሬ ድምፁን ብትሰሙ፣

3፥6 ቍ14፤ሮሜ5፥2፤11፥22፤1ቆሮ3፥16፤ 1ጢሞ3፥15፤ ዕብ1፥2፤ 4፥14፤6፥11፡ 8፡19፤7፥19፤11፥1 3፥7 ሐሥ28፥25፤ዕብ9፥8፤10፥15

[m]17 *ወይም ቍጣ ለመመለስ*

ያልነበረበት ጊዜ የለም፤ ሆኖም መከራ በተቀበለ ጊዜ የለበሰው ሥጋ (ትስብእቱ) ፍጽምናን አገኘ። ራሱን ከእኛ ጋር አንድ በማድረግ እኛ የሆነውን ሁሉ እርሱም ሆነ፤ ከዚህም የተነሣ ለኀጢአታችን የሚገባውን ዋጋ ሊከፍልልንና ሊራራልን የሚችል ሊቀ ካህናት ሆነልን።

2፥11 *ሰዎችን የሚቀድሰውና የሚቀደሱት*፤ ክርስቶስ ራሱን ከሰዎች ጋር አንድ ለማድረግ ሲል ሰው ሆነ፤ ስለ ሰው በመስቀል ላይ ራሱን መሥዋዕት አድርጎ በማቅረቡም የሰዎችን ሕይወት ዐደሰ። *ወድሞች ብሎ ሊጠራቸው*፤ ከኢየሱስ ጋር ያለን ወንድማማችነት፣ በቤዢና በተቤዢ መካከል ያለ ወንድማማችነት ሲሆን፣ በዚህም ፍጹም አንድነት አግኝተናል።

2፥12 *ስምህን ለወንድሞቼ እነግራቸዋለሁ*፤ ከመዝ 22፥22 ላይ የተወሰደ ጥቅስ ሲሆን፣ ይህም ጻድቁ የእግዚአብሔር ባሪያ መከራ መቀበሉንና ድል አድራጊ መሆኑን የሚገልጽ መዝሙር ነው። (የ"መዝ 22"ን መግቢያን ይመ)። እዚህ ላይ ቍልፉ ቃል "ወንድሞቼ" የሚለው ሲሆን፣ ቃሉ ከድል አድራጊው መሲሕ አንደበት የወጣ መሆኑን እናያለን።

2፥13 *በእርሱ እታመናለሁ፤* በእግዚአብሔር ላይ እውነተኛ መታመንን የሚገልጽ አባባል ሲሆን፣ ይህም ፍጹም ሆኖ የታየው በክርስቶስ ነው። ደግሞም ሰው ሊሆነው የሚገባው ነገር በትክክል የታየው በእርሱ ነው። *እነሆ፤ እኔና እግዚአብሔር የሰጠኝ ልጆች፤* ይህን ሥጕውም ልጅ ሲናገረው ይታያል። የአብ ልጆች የልጁ ወድሞች እንዲሆኑ ተሰጥተውታል ( ቍ 11 ይመ)።

2፥14 *በሞት ላይ ኀይል ያለውን*፤ ሰይጣን የሞትን ኀይል የሚይዘው ሰዎች ኀጢአት እንዲሠሩ ማሳትና ሞትን በሚያስከትለው የኀጢአት ቅጣት ሥር እንዲወድቁ ማድረግ እስከ ቻለ ድረስ ብቻ ነው (ሕዝ 18፥14፤ሮሜ5፥12-፤ 6፥23 ይመ)።

2፥15 *ነጻ*፤ 1ቆሮ 15፥54-57፤ ራእ 1፥18 ይመ።

2፥16 *የአብርሃምን ዘር*፤ ክርስቶስ የለበሰው የመላእክትን ተፈጥሮና ባሕርይ ሳይሆን፣ የአብርሃም ልጆች ተለይተው የሚታወቁበትን የሰዎችን ተፈጥሮና ባሕርይ ነው።

2፥17 *መሐሪና ታማኝ ሊቀ ካህናት*፤ ክርስቶስ ሰዎችን በእግዚአብሔር ፊት ወክሎ መቆም የሚችለው ከእነርሱ እንደ አንዱ ሲሆን ብቻ ነው። *የኀጢአትን ስርየት ... ለማስገኘት*፤ አማራጭ ትርጒሙን ይመ፤ እንዲሁም የዘሌ 16፥20-22፤ 17፥11፤ ማብ ይመ። ክርስቶስ ኀጢአተኞች ላይ የሚነደውን የእግዚአብሔርን ቍጣ ለመመለስ ከእነርሱ እንደ አንዱ መሆንና በእነርሱ ምትክ መሞት አለበት።

2፥18 *በተፈተነ ጊዜ*፤ የ4፥15 ማብ ይመ።

*3፥4-4፥13፤* የመዝሙር 95፥7-11 ማብ ነው። ክርስቶስ ከሙሴ በላይ መሆኑን በተጨባጭ የሚገልጽና አለመታዘዝና አለማመን የሚያስከትለውን ጥፋት የሚያስጠነቅቅ ክፍል ነው።

3፥1 *ተካፋዮች*፤ የቍ 14 ማብ ይመ። *የሰማያዊው ጥሪ፤* ከሰማይ የመጣና ወደ ሰማይ የሚመራ ግብዣ ነው። *ሐዋርያና*፤ "የተላከ" ማለት ነው (የማር 6፥30 እና የ1ቆሮ 1፥1 ማብ ይመ)። ኢየሱስ ወደዚህ ዓለም የመጣው ከአብ ተልኮ እንደሆነ ራሱ ተናግሮአል። ለምሳሌ (ማቴ 10፥40፤15፥24፤ ማር 9፥36፤ ሉቃ 9፥48፤ ዮሐ 4፥34፤5፥24፤30፤36-38፤6፥38 ይመ)። እርሱም ለሌሎቹ ሐዋርያትን የሚሰጥ ታላቅ ሐዋርያ ነው።

*3፥2*፤ እዚህ ላይ የሚነጻጸሩት ክርስቶስና ሙሴ ሲሆኑ፣ ሁለቱም ሕዝቡን እንዲመሩ ከአብ የተላኩ ቸው፤ አንደኛው ከፈርዖን ባርነት ነጻ አውጥቶ ወደ ተስፋይቱ ምድር የሚመራቸው ሲሆን፣ ሌላው ደግሞ የሚያምኑብትን ከዲያብሎስ ባርነት ነጻ አውጥቶ (2፥14-15) ተስፋ ወደ ተሰጣቸው የሰንበት ዕረፍት የሚመራቸው ነው (4፥3-9)። የሰንበት ዕረፍት የተባለው መንግሥተ ሰማይ ሊሆን ይችላል፤ ብዙዎች ግን ቃሉ የሚያመለክተው በክርስቶስ ቤዛነት የተገኘውን የደኅንነት ዕረፍት ነው ይላሉ። የቀረቡት ምሳሌዎች የሚያተኩሩት ታማኝ መጋቢ ሆኖ በመገኘት ላይ ነው።

3፥3 *ቤትን የሚሠራ ከቤቱ ይልቅ የሚበልጥ ክብር እንዳለው*፤ ኢየሱስ የቤቱ (የቤተ ሰቡ) ሠሪ ሲሆን፣ ሙሴ ግን ከቤተ ሰቡ እንደ አንዱ አባል የሚቈጠር ብቻ ነው።

3፥4 *ሁሉን የሠራ እግዚአብሔር ነው*፤ እዚህ ላይ ኢየሱስ ከአብ ጋር እኩል ሆኖ ቀርቦአል፤ ይህም ክርስቶስ ከሙሴ የሚበልጥ መሆኑን በግልጽ ያሳያል።

3፥5-6 *በእግዚአብሔር ቤት ሁሉ ላይ እንደ አንድ ታማኝ አገልጋይ ...በእግዚአብሔር ቤት ላይ እንደ ታማኝ ልጅ*፤ ክርስቶስ ከሙሴ እንደሚበልጥ በሁለት መንገድ ለማሳየት ተሞክሮአል፤ (1) ሙሴ አገልጋይ ሲሆን ክርስቶስ ግን ልጅ ነው፤ (2) ሙሴ የእግዚአብሔር ቤት አባል ማለትም ከቤተሰቡ አንዱ ሲሆን ክርስቶስ ግን የእግዚአብሔር ቤት ገዥ ነው።

3፥6 *እኛም ...ቤቱ ነን*፤ ቤቱ የተሠራው ቤተሰብ ከሆነው ከእግዚአብሔር ሕዝብ ነው፤ (ኤፌ 2፥19፤ 1ጴጥ 2፥5 ይመ)። *የምንተማመንበትንና የምንመካበትን ተስፋ አጥብቀን ብንይዝ* እስከ መጨረሻው ጸንቶ አለመቆም የእግዚአብሔር ልጅ አለመሆንን ሲያሳይ፣ እስከ መጨረሻው ጸንቶ መቆም ደግሞ የእርሱ ልጅ መሆንን የሚያሳይ ልዩ ምልክት ነው።

*3፥7-11*፤ ይህ ከመዝ 95፥7-11 ላይ የተወሰደው ጥቅስ በሙሴ አመራር ሥር ሆነው በምድረ በዳ ይጓዙ የነበሩትን የእስራኤላውያንን አሳፋሪ ታሪክ ባጭሩ የሚያቀርብ ነው። እዚህ ላይ

[8]በምድረ በዳ በፈተና ቀን፣
በዐመፅ እንዳደረጋችሁት፣
ልባችሁን አታደንድኑ።
[9]አባቶቻችሁ በዚያ ተፈታተኑኝ፤
መረመሩኝ፤ ያደረግሁትንም ሁሉ ለአርባ
ዓመት አዩ።
[10]በዚያም ትውልድ ላይ የተቈጣሁት ለዚህ ነበር፤
እንዲህም አልሁ፤ 'ልባቸው ሁልጊዜ ይስ
ታል፤
መንገዴንም አላወቁም፤'
[11]ስለዚህ በቍጣዬ እንዲህ ብዬ ማልሁ፤
"ወደ ዕረፍቴ ከቶ አይገቡም።"

[12]ወንድሞች ሆይ፤ ከእናንተ ማንም ከሕያው እግዚአብሔር የሚያስኰበልል፣ ኀጢአተኛና የማያምን ልብ እንዳይኖረው ተጠንቀቁ። [13]ነገር ግን ከመካከላችሁ ማንም በኀጢአት ተታሎ ልቡ እንዳይደነድን፣ "ዛሬ" እየተባለ ሳለ በየቀኑ እርስ በርሳችሁ ተጽናኑ። [14]በመጀመሪያ የነበረንን እምነት እስከ መጨረሻው አጽንተን ብንይዝ ከክርስቶስ ጋር ተካፋዮች እንሆናለን፤ [15]ይኸውም፣
"ዛሬ ድምጹን ብትሰሙ፣
በዐመፅ እንዳደረጋችሁት፣
አሁንም ልባችሁን አታደንድኑ" እንደተባ
ለው ነው።

[16]ሰምተው ያመፁት እነማን ነበሩ? ሙሴ ከግብፅ መርቶ ያወጣቸው ሁሉ አይደሉምን? [17]አርባ ዓመት የተቈጣውስ እነማንን ነበር? ኀጢአት ሠርተው ሬሳቸው በምድረ በዳ ወድቆ የቀረውን አይደለምን? [18]ያልታዘዙትን[ሠ] ካልሆነ በቀር ወደ ዕረፍቱ እንዳይገቡ የማለባቸው እነማን ነበሩ? [19]እንግዲህ ሊገቡ ያልቻሉት ካለማመናቸው የተነሣ እንደ ሆነ እንረዳለን።

3፥8 ቍ15፤ዕብ4፥7
3፥9 ዘኍ14፥33፤ ዘዳ1፥3፤ሐሥ7፥36
3፥11 ዘዳ1፥34፡35፤መዝ95፥7-11፤ ዕብ4፥3፡5
3፥12 ማቴ16፥16
3፥13 ኤር17፥9፤ ኤፌ4፥22፤ ዕብ10፥24፡25
3፥14 ቍ6፤ኤፌ3፥12
3፥15 ቍ7፡8፤ መዝ95፥7፡8፤ዕብ4፥7
3፥16 ዘኍ14፥2
3፥17 ዘኍ14፥29፤ መዝ106፥26፤ 1ቆሮ10፥5
3፥18 ዘኍ14፥20-23፤ ዘዳ1፥34፡35፤ዕብ4፥6
3፥19 መዝ78፥22፤ 106፥24፤ ዮሐ3፥36
4፥1 ዕብ12፥15
4፥2 1ተሰ2፥13
4፥3 ዘዳ1፥34፡35፤ መዝ95፥11፤ዕብ3፥11
4፥4 ዘፍ2፥2፡3፤ ዘፀ20፥11
4፥5 ቍ3፤መዝ95፥11
4፥6 ቍ11፤ዕብ3፥18
4፥7 መዝ95፥7፡8፤ ዕብ3፥7፡8፡15
4፥8 ኢያ22፥4፤ ዕብ1፥1

## የሰንበት ዕረፍት ለእግዚአብሔር ሕዝብ

**4** እንግዲህ ወደ ዕረፍቱ ለመግባት የተሰጠው ተስፋ አሁንም የተጠበቀ ስለ ሆነ፣ ከእናንተ ማንም ለዚያ ሳይበቃ እንዳይቀር እንጠንቀቅ፤ [2]ለእነዚያ እንደ ተሰበከ ለእኛም ደግሞ የምሥራቹ ቃል ተሰብኮልናልና። ነገር ግን ሰሚዎቹ ቃሉን ከእምነት ጋር ስላላዋሐዱት[ረ] አልጠቀማቸውም። [3]እኛ ያመነው ግን ወደዚያ ዕረፍት እንገባለን፤ እግዚአብሔርም፣
"ስለዚህ በቍጣዬ እንዲህ ብዬ ማልሁ፤
'ወደ ዕረፍቴ ከቶ አይገቡም' " ብሎአል።
ይሁን እንጂ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ የእርሱ ሥራ ተከናውኖአል። [4]ስለ ሰባተኛውም ቀን በአንድ ስፍራ፣ "በሰባተኛውም ቀን እግዚአብሔር ከሥራው ሁሉ ዐረፈ" ብሎአልና። [5]ቀደም ባለው ክፍል ደግሞ፣
"ወደ ዕረፍቴ ከቶ አይገቡም" ይላል።

[6]ወደ ዕረፍቱ ገና የሚገቡ አንዳንዶች አሉ፤ ቀድሞ የምሥራቹ ቃል የተሰበከላቸው ባለመታዘዛቸው ምክንያት ወደ ዕረፍት አልገቡም። [7]ስለዚህ እግዚአብሔር፣ "ዛሬ" ብሎ እንደ ገና አንድን ቀን ወሰነ፤ ይህም ከብዙ ዘመን በኋላ በዳዊት በኩል፣
"ዛሬ ድምፁን ብትሰሙ፣
ልባችሁን አታደንድኑ"
ተብሎ ቀደም ሲል እንደተነገረው ነው።
[8]ኢያሱ ዕረፍትን ሰጥቶአቸው ቢሆን ኖሮ፣ ከዚያ በኋላ እግዚአብሔር ስለ ሌላ ቀን ባልተ

*[ሠ]18 ወይም ያላመኑትን*
*[ረ]2 ወይም ከታዘዙት ጋር ስላላመኑ*

ሦስት ዘመኖች ወይም ጊዜዎች ተጠቅሰዋል፤ እነዚህም ከግብጽ መውጣት የተፈጸመበት፣ መዝሙረኛው የነበረበትና የዕብራውያን መልእክት የተጻፈበት ናቸው። መዝሙረኛው በሙሴ አመራር ሥር የነበሩ እስራኤላውያንን ምሳሌ አድርጎ በመውሰድ፣ በእርሱ ዘመን ለሚገኙ እስራኤላውያን አለማመንና አለመታዘዝ የሚያስከትለውን ቅጣት ለማስጠንቀቅ ተጠቅሞበታል። ልክ እንዲሁ የዕብራውያን መልእክት ጸሓፊም የመዝሙረኛው ማስጠንቀቂያ ለተደራሲያኑና በዚህም ዘመን የሚገኙ የእግዚአብሔር ሰዎችን የሚመለከት መሆኑን ይገልጻል።

3፥12 *ከእናንተ ማንም ከሕያው እግዚአብሔር የሚያስኰበልል፤* ከግብጽ የወጡት አንዳንድ እስራኤላውያን እንዳደረጉት፣ ዐመፀኛ ሆኖ ከእግዚአብሔር መኰብለል (ቃል በቃል ሲተረጎም "ከሓዲ መሆን" ማለት ነው) ከሕይወት ኰብልሎ ሞትን መምረጥ ማለት ነው።

3፥13 *"ዛሬ" እየተባለ ሳለ፤* 4፥7 ይመ። ይህ ቀን አሁንም የእግዚአብሔር የጸጋ ቀንና በእርሱም ለማመን የተመረጠ ይሁን እንጂ ይህ ሁኔታ ገደብ የለሽ አይደለም።

3፥14 *ከክርስቶስ ጋር ተካፋዮች፤* የእርሱና የበረከቱ ተካፋይ መሆን ነው (ከቍ1 ጋር ያነጻጽሩ)። *በመጀመሪያ የነበረንን እምነት እስከ መጨረሻው አጽንተን ብንይዝ፤* አንድ ሰው ድነት እንደተቀበለ ማረጋገጥ የሚችለው፣ በእምነቱ እስከ መጨረሻው ድረስ መዝለቅ የቻለ እንደሆነ ነው። በዚህ ዐይነት ጸንቶ ከክርስቶስ ጋር ተካፋይ የሚሆኑት ሰዎች እነማን እንደ ሆኑ የሚታወቁት በእንዲህ ያለው ጽናት ነው (የቍ 6 ማብ ይመ)።

*3፥16-19፤* የመልእክቱ ጸሓፊ የጀመረውን ገለጻ የሚቀጥለው እርስ በርስ የቀያያዙ ጥያቄዎችን በማንሣት ነው። እዚህ ላይ እንዲታይ የተፈለገው እውነት ወደ ከነዓን ለመግባት ያልቻሉት እስራኤላውያን፣ እግዚአብሔር ስለ ተስፋዪቱ ምድር የገባውን ቃል በጆሮአቸው የሰሙና እግዚአብሔር የሰጠውን ተስፋ (ቍ 19)፣ ያላመኑ መሆናቸውን ነው፤ ይህም ድርጊት እንደ ዐመፅ (ቍ 6)፣ ኀጢአትና (ቍ 17) አለመታዘዝ (ቍ18) ተቈጥሮባቸዋል። በዚህም ምክንያት እግዚአብሔር ከቍጣው የተነሣ በወቅቱ በነበሩት በእስራኤላውያን ትውልድ ፊት የከነዓንን በሮች ዘጋ (ዘኍ 14፥21-35)። በመጀመሪያው ምእተ ዓመት የነበሩ የዕብራውያን መልእክት ተደራሲዎችም ተመሳሳይ የሆነ መንፈሳዊ ችግር ገጥሞአቸው ነበር።

4፥1 *እንግዲህ ወደ ዕረፍቱ ለመግባት የተሰጠው ተስፋ አሁንም የተጠበቀ ስለሆነ፤* ድነትን አሁንም፤ ማግኘት ይቻላል። ወደ ዕረፍቱ የሚለው ሐረግ የሚያመለክተው እስራኤላውያን ከነዓን ሲገቡ የሚያገኙትን ዕረፍት አይደለም። ይህ በኢያሱ መሪነት ያገኙት ዕረፍት ጊዜአዊና ምድራዊ (ቍ8 ይመ እንዲሁም የኢያሱን 1፥13 ማብ ይመ) ሲሆን የሚያመለክተውም ወደፊት የሚመጣውን ዘላለማዊና ሰማያዊ ዕረፍት ነው።

4፥3 *እኛ ያመነው ... ወደዚያ ዕረፍት እንገባለን፤* ወደ ምድራዊቷ ከነዓን ለመግባት እግዚአብሔር የተሰጠውን ተስፋ ማመን እንደሚያስፈልግ ሁሉ፣ ወደ ድነቱ ዕረፍት መግባት የሚቻለውም ኢየሱስ ክርስቶስንና የፈጸመውን የማዳን ሥራ በማመን ብቻ ነው። *ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ የእርሱ ሥራ ተከናውኖአል፤* እግዚአብሔር የመፍጠር ሥራውን ፈጽሞ በሰባተኛው ቀን ዐረፈ (ቍ 4፤ ዘፍ 2፥2 ይመ)፤ በመሆኑም ዕረፍቱ ቀድሞውኑ የተረጋገጠ ነው። እግዚአብሔር እንድንገባበት የጠራን ዕረፍት (ቍ 10-11)፣ የእኛ ዕረፍት ሳይሆን የእርሱ ዕረፍት ነው፤ እርሱም ይህን ዕረፍት እንድንካፈል ጋበዘን።

*4፥6-8* እስራኤላውያን በኢያሱ መሪነት ወደ ከነዓን ምድር ቢገቡም፣ የገቡት ግን ከፊልና ጊዜአዊ ወደ ሆነው የእግዚአብሔር ዕረፍት ነው። በመዝ 95፥7-8 ላይ እንደተመለከተው ግብዣው የሚቀጥል በመሆኑ፣ ወደዚያ ዕረፍት መግባቱ የመጨረሻ አይደለም።

4፥7 *"ዛሬ" ብሎ፤* የ3፥13 ማብ ይመ።

ናገረ ነበር:: 9ስለዚህ የሰንበት ዕረፍት ለእግዚአብሔር ሕዝብ ገና ቀርቶለታል፤ 10ምክንያቱም ወደ እግዚአብሔር ዕረፍት የሚገባ ሁሉ፣ እግዚአብሔር ከሥራው እንዳረፈ፣ እርሱም ደግሞ ከሥራው ያርፋል:: 11እንግዲህ ማንም የእነዚያን አለመታዘዝ ምሳሌ ተከትሎ እንዳይወድቅ ወደዚያ ዕረፍት ለመግባት እንትጋ::

12የእግዚአብሔር ቃል ሕያውና የሚሠራ ነውና፤ በሁለት በኩል ስለት ካለው ሰይፍ ሁሉ ይልቅ ስለታም ነው፤ ነፍስንና መንፈስን፣ ጅማትንና ቅልጥምን እስኪለያይ ድረስ ዘልቆ ይወጋል፤ የልብንም ሐሳብና ምኞት ይመረምራል:: 13ከእግዚአብሔር ዐይን የተሰወረ ምንም ፍጥረት የለም፤ ስለ ራሳችን መልስ መስጠት በሚገባን በእርሱ ፊት ሁሉም ነገር የተራቈተና የተገለጠ ነው::

## ታላቁ ሊቀ ካህናት ኢየሱስ

14እንግዲህ ወደ ሰማያት ያረገ[ሀ] ታላቅ ሊቀ ካህናት የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ስላለን፣ እምነታችንን አጥብቀን እንያዝ:: 15በድካማችን የማይራራልን ሊቀ ካህናት የለንምና፤ ነገር ግን እንደ እኛ በማንኛውም ነገር የተፈተነ ሊቀ ካህናት አለን፤ ይሁን እንጂ ምንም ኀጢአት አልሠራም:: 16እንግዲህ ምሕረትን እንድንቀበልና በሚያስፈልገንም ጊዜ የሚረዳንን ጸጋ እንድናገኝ፣ ወደ ጸጋው ዙፋን በእምነት እንቅረብ::

5 እያንዳንዱ ሊቀ ካህናት ከሰዎች መካከል ይመረጣል፤ የእግዚአብሔርም በሆነው ነገር ላይ ሰዎችን በመወከል ለኀጢአት የሚሆነውን መባንና መሥዋዕትን ለማቅረብ ይሾማል:: 2እርሱ ራሱ ድካም ያለበት በመሆኑ፣ አላዋቂ ለሆኑትና ለሚባዝኑት ሊራራላቸው ይችላል:: 3ስለራሱ ኀጢአትና ስለ ሌሎች ሰዎች ኀጢአት መሥዋዕት ማቅረብ የተገባው በዚሁ ምክንያት ነው::

4አሮን እንደ ተጠራ በእግዚአብሔር መጠራት አለበት እንጂ፣ ይህን ክብር ለራሱ የሚወስድ ማንም የለም:: 5እንዲሁም ክርስቶስ ሊቀ ካህናት የመሆንን ክብር ለራሱ አልወሰደም፤ ነገር ግን እግዚአብሔር፣

"አንተ ልጄ ነህ፤
እኔ ዛሬ አባት ሆንሁህ"[ለ] አለው::

6እንዲሁም በሌላ ስፍራ፣
እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት፣
አንተ ለዘላለም ካህን ነህ" ይላል::

7ኢየሱስ በዚህ ምድር በኖረበት ዘመን

4፥10 ቍ4፤ዘሌ23፥3፤ ራእ14፥13
4፥11 ቍ6፤ዕብ3፥18
4፥12 ኢሳ55፥11፤ ኤር23፥29፤ ማር4፥14፤ሉቃ5፥1፤ 11፥28፤ዮሐ10፥35፤ ሐሥ7፥38፤12፥24፤ 1ቆሮ14፥24:25፤ኤፌ 6፥17፤1ተሰ2፥13፤ 2ጢ2፥9፤ 1ጴጥ1፥23፤1ዮሐ2፥14፤ ራእ1፥2:9:16
4፥13 መዝ33፥13-15፤ ምሳ5፥21፤ኤር16፥17፤ 23፥24፤ዳን2፥22
4፥14 ማቴ4፥3፤ ዕብ2፥17፤3፥1፤6፥20፤ 8፥1፤9፥24
4፥15 2ቆሮ5፥21፤ ዕብ2፥17:18
4፥16 ኤፌ3፥12፤ ዕብ7፥19

5፥1 ዕብ2፥17፤7፥27፤ 8፥3፤9፥9
5፥2 ኢሳ29፥24፤ ዕብ2፥18፤4፥15፤7፥28
5፥3 ዘሌ9፥7፤16፥6፤ ዕብ7፥27፤9፥7
5፥4 ዘፀ28፥1፤ ዘኍ14፥40፤18፥7
5፥5 መዝ2፥7፤ ማቴ3፥17፤ዮሐ8፥54፤ ዕብ1፥1፤2፥17

5፥6 ቍ10፤ዘፍ14፥18፤መዝ110፥4፤ዕብ6፥20፤7፥1-22 5፥7 መዝ22፥24፤ማቴ27፥46:50፤ማር14፥36፤ሉቃ22፥41-44፤23፥46

[ሀ]14 ወይም ወደ ሰማይ የገባ
[ለ]5 ወይም ወልጄሃለሁ::

4፥9 *ስለዚህ የሰንበት ዕረፍት ... ገና ቀርቶለታል፤* ወደ እግዚአብሔር ዕረፍት መግባት የሚቻለው በልጁ በማመን ብቻ ነው::

4፥10 *ከሥራው ያርፋል፤* እግዚአብሔር የሥነ ፍጥረት ሥራውን ጨርሶ እንዳረፈ፣ አማኞችም ድነትን በገዛ ሥራቸው ለማግኘት የሚያደርጉት ጥረት አቁመው ክርስቶስ በመስቀል ላይ ሠርቶ በፈጸመው ሥራ ያርፋሉ:: አንዳንድ ሊቃውንት እንደሚናገሩት እዚህ ላይ ጸሓፊው የሚናገረው አማኞች ስለሚያገኙት የመጨረሻው ዕረፍት ነው (ራእ 14፥13 ይመ)::

4፥11 *እንትጋ፤* ድነትን በሥራ እንድናገኝ የቀረበ ጥሪ ሳይሆን፣ ወደ ድነቱ ዕረፍት በእምነት እንድንገባ እንጂ እስራኤላውያን በምድረ በዳ የፈጸሙትን አሳዛኝ ምሳሌ እንዳንከተል የተሰጠ ምክር ነው::

*4፥12-13፤* በቍ 11 ላይ የተሰጠው ምክር በሚገባ ማጤን ያስፈለገበትን ምክንያት የሚገልጽ ነው::

4፥12 *የእግዚአብሔር ቃል፤* የእግዚአብሔር እውነት የተገለጠው በኢየሱስ ነው (እርሱም ሥጋ የበለበሰው ቃል ነው፤ (ዮሐ 1፥1፤14 ይመ)፤ እዚህ ላይ የተነገረው "ቃል" የተገለጠው በቃል ማለት በአንደበት ነው:: ይህ ብርቱ ኀይል ያለው የእግዚአብሔር ቃል ሕያው በመሆኑ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ሊፈጽም እንደሚችል በብሉይና በአዲስ ኪዳን ተገልጦአል (መዝ 107፥20፤147፥18፤ኢሳ40፥8፤55፥11፤ገላ3፥8፤ኤፌ5፥26፤ያዕ1፥18፤ 1ጴጥ1፥23 ይመ):: የዕብራውያን መልእክት ጸሓፊም ሲናገር፣ ይህ ቃል ሁሉን በሚያይ ዐይን ስውር በሆነው ውስጣዊ አካላችን ዘልቆ በመግባት መመርመር የሚችል ሕያው ኀይል ነው:: *ነፍስንና መንፈስን፣ ጅማትንና ቅልጥምን፤* የሰውን ሁለንተናና ጥልቅ የሆነውን ውስጣዊ ማንነቱን የሚገልጽ ነው::

4፥13 *ከእግዚአብሔር ዐይን የተሰወረ ምንም ፍጥረት የለም፤* የመልእክቱ ጸሓፊ ቃሉ የሚሠራው ሥራና እግዚአብሔር የሚሠራው ሥራ አንድና ተመሳሳይ እንደ ሆኑ አድርጎ አቅርቦአቸዋል፤ በእርግጥም ደግሞ አንድና ተመሳሳይ ናቸው::

*4፥14-7፥28፤* የመዝ 110፥4 ማብራሪያ ሲሆን፣ ክርስቶስ የሚሻል ክህነት ስላለው ከአሮን በላይ መሆኑን በአጽንዖት የሚገልጽ ክፍል ነው::

4፥14 *ታላቅ ሊቀ ካህናት፤* 2፥17፤3፥1 ይመ:: የመልእክቱ ጸሓፊ የክርስቶስ ክህነት ከአሮን ክህነት የሚበልጥ መሆኑን ለመግለጽ፣ ረጅም ማብራሪያውን እዚህ ላይ ይጀምራል:: *ወደ ሰማያት፤* ከአሮን ወገን የሆኑት ሊቀ ካህናት በስርየት ቀን በሕዝቡ ፊት አልፈው ወደ ቅድስተ ቅዱሳን እንደሚገቡ ሁሉ (ዘሌ 16፥14፤17 ይመ)፣ ኢየሱስም ቆመው በሚያዩት ደቀ መዛሙርቱ ፊት ወደ ሰማይ ማለትም ወደ ሰማያዊቷ ቤተ መቅደስ ዐረገ፤ ይህም የቤዛነት ሥራውን እንደ ፈጸመ ያሳያል:: (ሐሥ 1፥9-11):: *እምነታችንን አጥብቀን እንያዝ፤* የመልእክቱ ተደራሲዎች ከያዙት እምነት ለማፈግፈግ የዳዳቸው ይመስላል፡ (ተመሳሳይ ምክር መስጠቱን በ2፥1፤3፥6፤14 ላይ ይመ)::

4፥15 *ነገር ግን እንደ እኛ በማንኛውም ነገር የተፈተነ፤* 2፥18 ይመ:: የመልእክቱ ጸሓፊ በክርስቶስና በእኛ ላይ የደረሰውን ፈተና ጎን ለጎን አስቀምጦ ያነጻጽራል፤ ክርስቶስ፣ በእኛ ላይ የደረሰውን ፈተና ሁሉ ባይቀበልም፣ እንደ እኛ በሁሉም ረገድ ተፈትኖአል:: *ይሁን እንጂ ምንም ኀጢአት አልሠራም፤* የክርስቶስ መፈተን ከእኛ የሚለይበት ነገር ቢኖር በውጤቱ ብቻ ነው፤ ይኸውም እርሱ እንደ እኛ በተፈትነ ጊዜ በፈተናው አልወደቀም (ማቴ 4፥1-11 ይመ)::

*5፥1-4፤* ሊቀ ካህናት ሆኖ ለማገልገል ሁለት መመዘኛዎችን ማሟላት ያስፈልጋል፤ (1) የሚመረጠው ሰው "ከሰዎች መካከል" (ቍ 1) መሆን አለበት፤ እንዲህ ከሆነ ሰዎችን ወክሎ በእግዚአብሔር ፊት መቆም ይችላል:: (2) "በእግዚአብሔር መጠራት አለበት" (ቍ 4)::

5፥1 *መባንና መሥዋዕትን፤* 8፥3፤9፥9 ተመልከት፤ እንዲሁም የዘሌ 1፥2፤2፥1 ማብ ይመ::

5፥2 *አላዋቂ ለሆኑትና ለሚባዝኑት፤* ኢሳ 53 6 የመ:: ባለማወቅ የሚፈጸመውን ኀጢአት (በዘሌ 4፤ዘኍ15፥27-29 እንደ ተጠቀሰው ዐይነት)፣ እግዚአብሔርን በመናቅ ሆን ብሎ ከሚሠራው ኀጢአት ጋር ያነጻጽሩ (ዘኍ 15፥30-31 ይመ፤ እንዲሁም ከዕብ 6፥4-6፤10፥26-31 ጋር ያነጻጽሩ)::

5፥4 *ይህን ክብር ለራሱ የሚወስድ ማንም የለም፤* ክርስቶስ በነበረበት ዘመን የሊቀ ካህናት ቢሮ በአንድ ቤተሰብ ቍጥጥር ሥር ነበር::

5፥5 *ክርስቶስ ሊቀ ካህናት የመሆንን ክብር ለራሱ አልወሰደም፤* እዚህ ላይ የተጠቀሱት ሁለት ትንቢታዊ ምንባቦች እንደሚያመለክቱት፣ ልጁ የተሾመው በአብ ነው (መዝ 2፥7፤110፥4)፤ ደግሞም ሊቀ ክህነቱ እንደ አሮን ሹመት ሳይሆን "እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት" (ቍ 6) ነው:: *እኔ ዛሬ አባት ሆንሁህ፤* የ1፥5፤ እና መዝ 2፥7-9 ማብ ይመ፤ ከሮሜ 1፥4 ጋር ያነጻጽሩ::

5፥7 *ኢየሱስ በዚህ ምድር በኖረበት ዘመን፤* እዚህ ላይ ለማመልከት የተፈለገው ዋናው ነገር ክርስቶስ በጌቴሴማኒ የአት

ከሞት ሊያድነው ወደሚችለው ጸሎትንና ልመናን ከታላቅ ጩኸትና ከእንባ ጋር አቀረበ፤ ፍጹም ትሑት ሆኖ በመታዘዙም ጸሎቱ ተሰማለት። 8የእግዚአብሔር ልጅ ቢሆንም እንኳ፣ ከተቀበለው መከራ መታዘዝን ተማረ፤ 9በዚህም ፍጹም ሆኖ ከተገኘ በኋላ፣ እርሱን ለሚታዘዙ ሁሉ የዘላለም ድነት ምክንያት ሆነላቸው፤ 10እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመትም ሊቀ ካህናት ተብሎ በእግዚአብሔር ተሾመ።

### በእምነት ስላለመጽናት የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

11ስለዚህ ጉዳይ የምንናገረው ብዙ ነገር አለን፤ ነገር ግን ለመማር ዳተኛ ስለ ሆናችሁ ለማስረዳት አስቸጋሪ ነው። 12በዚህ ጊዜ አስተማሪዎች ልትሆኑ ሲገባችሁ፣ ገና የእግዚአብሔርን ቃል የመጀመሪያ ትምህርት የሚያስተምራችሁ ሰው ያስፈልጋችኋል፤ የሚያስፈልጋችሁም ጠንካራ ምግብ ሳይሆን ወተት ነው። 13ወተት የሚጋት ሁሉ ሕፃን ስለሆነ፣ ከጽድቅ ትምህርት ጋር ገና አልተዋወቀም። 14ጠንካራ ምግብ ግን መልካሙን ከክፉው ለመለየት ራሳቸውን ባስለመዱ፣ ለበሰሉ ሰዎች ነው።

6 ስለዚህ ስለ ክርስቶስ የተሰጠውን የመጀመሪያ ትምህርት ትተን ወደ ብስለት እንሂድ፤ ከሞተ ሥራ ንስሓ ስለ መግባትና* በእግዚአብሔር ስለ ማመን እንደ ገና መሠረትን አንጣል፤ 2እንዲሁም ስለ ጥምቀቶች፣ እጆችን ስለ መጫን፣ ስለ ሙታን ትንሣኤና ስለ ዘላለም ፍርድ ትምህርት እንደ ገና አንመሥርት። 3እግዚአብሔር ቢፈቅድ ይህን እናደርጋለን።

4አንድ ጊዜ ብርሃን የበራላቸውን፣ ሰማያዊውን ስጦታ የቀመሱትን፣ ከመንፈስ ቅዱስ ተካፋዮች የሆኑትን፣ 5መልካሙን የእግዚአብሔር ቃልና የሚመጣውን ዓለም ኀይል የቀመሱትን፣ 6በኋላ ግን የካዱትን እንደ ገና ወደ ንስሓ መመለስ አይቻልም፤ ምክንያቱም እነርሱ ለገዛ ጥፋታቸው የእግዚአብሔርን ልጅ እንደገና ይሰቅሉታል፤ ያዋርዱታልም።

7ዘወትር በእርሷ ላይ የሚወርደውን ዝናብ የምትጠጣና ለሚያርሷትም ፍሬ የምትሰጥ መሬት ከእግዚአብሔር በረከትን ትቀበላለች።

*1 *ወይም ከከንቱ ሥርዐት*

5÷8 ፊል2÷8፤ ዕብ1÷2
5÷9 ዕብ2÷10
5÷10 ቊ5:6፤ ዕብ2÷17
5÷12 1ቆሮ3÷2፤ ዕብ6÷1፤1ጴጥ2÷2
5÷13 1ቆሮ14÷20
5÷14 ኢሳ7÷15፤ 1ቆሮ2÷6
6÷1 ፊል3÷12-14፤ ዕብ5÷12፤9÷14
6÷2 ዮሐ3÷25፤ ሐሥ2÷24፤6÷6፤ 17÷18:32
6÷3 ሐሥ18÷21
6÷4 ገላ3÷2፤ኤፌ2÷8፤ ዕብ10÷32
6÷5 መዝ34÷8፤ ዕብ4÷12
6÷6 ማቴ4÷3፤ 2ጴጥ2÷21፤1ዮሐ5÷16

ክልት ስፍራ የደረሰበትን ሥቃይ ነው። *ከሞት ሊያድነው ወደሚችለው፤* ወደ አባቱ ነው። ኢየሱስ ከእርሱ እንዲያልፍ የፈለገው በሥጋው የሚቀበለውን መከራና ሞት ሳይሆን የሰዎችን ኀጢአት በመሸከሙ የሚደርስበትን እንደበት ሊገልጸው የማይቻለውን ሥቃይ ነው (ማቴ 27÷46 ይመ)። ምንም እንኳ የመከራው ጽዋ ከእርሱ እንዲወገድ ቢለምንም፣ የአባቱን ፈቃድ ለመፈጸም ካለው ቁርጥ አቋም ግን ከቶ አላመነታም (ማቴ 26÷36-46 ይመ)። *ተሰማለት፤* አብ ትንሣኤ በመስጠት ጸሎቱ መልስ እንዲያገኝ አድርጎአል።

5÷8 *ከተቀበለው መከራ መታዘዝን ተማረ፤* "ፍጹም" (ቊ 9) ሊሆን የቻለው በተቀበለው መከራ (የ2÷10 ማብ ይመ)፤ ማለትም በምድረ በዳ በተቀበለው ፈተናና በመስቀል ላይ በተሸከመው መከራ ነው። ምንም እንኳ የእግዚአብሔር ዘላለማዊ ልጅ ቢሆንም፣ ሥጋ የለበሰ ልጅ እንደ መሆኑ፣ መታዘዝን መማር ያስፈልገዋል፤ ይህ የሆነው ያልታዘዘበት ጊዜ ስለ ነበር ሳይሆን፣ ከዚህ በፊት ያላሳየውን መታዘዝ እንዲያሳይ በመጠራቱ ነው። የደረሰበት ፈተና እውነተኛ ከመሆኑም በላይ ውጊያውን በአሸናፊነት ለመወጣት እጅግ አስቸጋሪ ነበር፤ ይሁን እንጂ አዳም የሳተበትንና የወደቀበትን ነገር ኢየሱስ ተቋቁሞ ድል አደረገ። በዚህ ዐይነት ሰብአዊ ማለትም ሰው መሆኑ "ፍጹም ሆነ" (ቊ 9)፤ ፍጹም በመሆኑም "ዘላለማዊ ቤዛነትን ሊያስገኝ" (9÷12 ይመ) ቻለ።

5÷11 *ስለዚህ ጉዳይ የምንናገረው ብዙ ነገር አለን፤* "እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት" (ቊ10) ስላለው፣ ስለ ክርስቶስ ዘላለማዊ ክህነት ነው። *ለመማር ዳተኛ ስለ ሆናችሁ፤* በክርስትና ሕይወታቸው እያደጉ መሄድ ሲገባቸው ለመንፈሳዊ ነገር ልበ ሙትና ዳተኞች ሆነዋል (6÷12)።

5÷12 *በዚህ ጊዜ፤* አዲስ አማኞች አይደሉም። *የእግዚአብሔርን ቃል የመጀመሪያ ትምህርት፤* እነዚህ ትምህርቶች በ6÷1-2 ላይ ተዘርዝረዋል (የዚህን ማብ ይመ)። በክርስትና ሕይወታቸው እየበሰሉ ለመሄድ ጉዞ ከጀመሩ በኋላ እየተንሸራተቱ ቀድሞ ወደነበሩበት ስፍራ ይመለሳሉ። *ጠንካራ ምግብ* በምዕ 7 ላይ እንደሚገኘው ከባድ ትምህርት ነው።

5÷14 *ለበሰሉ ሰዎች፤* በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ያደጉና የጠራ ማስተዋልና የማመዛዘን ችሎታ ያላቸው ክርስቲያኖች ናቸው። ያላቸው *መልካሙን ከክፉው ለመለየት፤* በሥጋዊም ሆነ በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ሕፃናት የሆኑ ሰዎች እንዲህ ማድረግ አይችሉም።

6÷1-2 *እንደ ገና መሠረትን አንጣል፤* እዚህ ላይ ስድስት መሠረታዊ አስተምህሮች ተወሥተዋል፤ እነዚህም (1) *ንስሓ፤* አንድ ሰው ከኀጢአቱና ከንቱ ከሆነ ሥርዐት (አማራጭ ትርጒሙን ይመ) እንዲመለስ የሚያደርግ ፍጹም ለውጥ ነው። (2) *በእግዚአብሔር ስለ ማመን፤* የንስሐ ሌላው ገጽታ ነው። ንስሓ ከኀጢአት ጨለማ መመለስ እንደ ሆነ ሁሉ፣ እምነት ደግሞ ወደ እግዚአብሔር ብርሃን መመለስ ነው። (3) *ስለ ጥምቀቶች፤* የመልእክቱ ተደራሲዎች የሚያውቁአቸው ልዩ ልዩ ጥምቀቶች ሳይሆኑ አይቀሩም፤ እነርሱም አሕዛብ የአይሁድ እምነት ሲቀበሉ የሚጠመቁት ጥምቀት፣ መጥምቁ ዮሐንስ ያጠመቀው ጥምቀትና ኢየሱስ ያዘዘው ጥምቀት ናቸው (ማቴ28÷19)። (4) *እጆችን ስለ መጫን፤* አንዳንድ ጊዜ ከጥምቀት በኋላ የሚፈጸም ሥርዐት ነው (ሐሥ 8÷16-17፤19÷5-6)። አለበለዚያ እጅ የሚጫነው ሰዎችን ለተለየ አገልግሎት ለመሾም ወይም ለመላክ (ሐዋ 6÷6፤13÷3፤ 1ጢሞ 5÷22፤ 2ጢሞ 1÷6 ይመ)፣ ወይም ሕሙማንን ለመፈወስና (ማር 6÷5፤ 16÷18፤ ሉቃ 4÷40፤ ሐሥ 28÷8 ይመ) ቡራኬ ለመስጠት (ማቴ 19÷13-15 ይመ) ነው። (5) *ስለ ሙታን ትንሣኤና፤* በመጨረሻው ቀን ሰዎች ሁሉ የሚያገኙትን ትንሣኤ ነው (ዮሐ 5÷25-29፤11÷25፤ 2ቆሮ 4÷14 ይመ)። (6) *ስለ ዘላለም ፍርድ፤* የእግዚአብሔርን የማዳን ጸጋ በመናቅ በክፉ መንገዳቸው የቀጠሉትን ነው።

6÷1 *ስለ ክርስቶስ የተሰጠውን የመጀመሪያ ትምህርት፤* የ5÷12 ማብ ይመ።

*6÷3፤* በእግዚአብሔር ላይ መታመንን የሚገልፅ የተለመደ አባባል ነው (1ቆሮ 16÷17 ጋር ያነጻጽሩ)። የሰዎችን አእምሮና ልብ መክፈትና መንፈሳዊ ብስለትን ማምጣት የሚችል ጌታ ብቻ ነው።

*6÷4-6፤* ይህን ክፍል አስመልክቶ የሚሰጡት የታወቁት ትርጓሜዎች ከዚህ የሚከተሉት ናቸው፤ (1) ክፍሉ የሚናገረው በእርግጥ ድነታቸውን ስላጡ ሰዎች ነው። (2) በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ብስለት ያላሳዩትን የዕብራውያን ክርስቲያኖች (5÷11-14) በነገር ሁሉ እያደጉና እየበሰሉ መሄድ እንዳለባቸው የሚያሳስብ ሲሆን (በቊ1 ይመ)፣ ይህ ሳይሆን ቢቀር እግዚአብሔር እንደሚቀጣቸውና እንደሚፈርድባቸው (ቊ7-8 ይመ) የሚገልጽ ግምታዊ ሐሳብ ነው። (3) ክርስቲያኖች ነን ሲሉ የነበሩትንና በኋላ ግን ክህደታቸው፣ እምነታቸው ቀድሞውኑ እውነተኛ እንዳልሆነ ያሳየውን የሚያመለክት ነው (ከ1ዮሐ2÷19 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህ አመለካከት ከምዕ3-4 ያለውን ክፍል የሚያየው እንደ ማስጠንቀቂያ ሲሆን፣ ለዚህም መሠረት ያደረገው እስራኤላውያን በምድረ በዳ ሳሉ የፈሙትን ዐመፅ ነው። እስራኤል የተስፋዪቱን ምድር ከሰለለችና ፍሬዋንም ከቀመሰች በኋላ ወደ ምድሪቱ መግባት እንዳልቻለች ሁሉ፣ እኛም አማኞች ነን የሚሉት የዕብራውያን ክርስቲያኖች ከበራላቸው "ብርሃን" በልበ ደንዳናነት ዘወር ካሉ ንስሓ መግባት አይችሉም።

6÷5 *የሚመጣውን ዓለም፤* ማር 10÷30 እና ማብ ይመ፤ እንዲሁም 1ጢሞ 6÷19 ይመ።

*6÷7-8፤* ከፍ ብሎ የተሰጠውን ማስጠንቀቂያ በአጭሩ የሚገልጽ ሥዕላዊ ምሳሌ ነው (ዮሐ 15÷5-6፤ 2ጴጥ 2÷20-21፤

[8]ነገር ግን እሾህና አሜከላ የምታበቅል መሬት ዋጋ ቢስ ትሆናለች፤ መረገሚያ ዋም ተቃርቦአል፤ መጨረሻዋም በእሳት መቃጠል ነው። 

[9]ወዳጆች ሆይ፤ ምንም እንኳ እንደዚህ ብንናገርም፣ ከድነታችሁ ጋር የተያያዘ ታላቅ ነገር እንዳላችሁ እርግጠኞች ነን። [10]እግዚአብሔር ዐመፀኛ አይደለም፤ እርሱ ሥራ ችሁን እንዲሁም በፊትም ሆነ አሁን ቅዱ ሳንን በመርዳት ስለ ስሙ ያሳያችሁትን ፍቅር አይረሳም። [11]የተሰጠው ተስፋ እስኪ ፈጸም ድረስ እያንዳንዳችሁ እንዲህ ያለውን ትጋት እስከ መጨረሻ እንድታሳዩ እንመ ኛለን። [12]በእምነትና በትዕግሥት የተስፋ ውን ቃል የሚወርሱትን እንድትመስሉ እንጂ ዳተኞች እንድትሆኑ አንፈልግም።

## የእግዚአብሔር የተስፋ ቃል እርግጠኛነት

[13]እግዚአብሔር ለአብርሃም ተስፋ በሰጠው ጊዜ፣ የሚምልበት ከእርሱ የሚበልጥ ሌላ ባለ መኖሩ፣ በራሱ ማለ፤ [14]እንዲህም አለ፤ “በእርግጥ እባርክሃለሁ፤ ዘርህንም አበዛዋለሁ።” [15]አብርሃምም በትዕግሥት ከጠበቀ በኋላ የተ ሰጠውን ተስፋ አገኘ።

[16]ሰዎች ከእነርሱ በሚበልጥ ይምላሉ፤ መሐላውም የተባለውን ነገር ስለሚያጸና፣ በመካከላቸው የተነሣው ክርክር ሁሉ ይወ ገዳል። [17]እግዚአብሔር የማይለወጥ ዐላማውን ለተስፋው ቃል ወራሾች ግልጽ ለማድረግ ስለፈለገ፣ በመሐላ አጸናው፤ [18]እግዚአብሔር ከቶ ሊዋሽ አይችልም፤ እርሱ በሁለት በማ ይለወጡ ነገሮች በፊታችን ያለውን ተስፋ ለመያዝ ወደ እርሱ ለሸሸን ለእኛ ብርቱ መጽናናት እንድናገኝ አድርጎአል። [19]እኛም የነፍስ መልሕቅ የሆነ ጽኑና አስተማማኝ ተስፋ አለን፤ ይህም ተስፋ ከመጋረጃው በስተጀርባ ወዳለው ውስጠኛ መቅደስ ይገባል። [20]ይህም ስፍራ ኢየሱስ ስለ እኛ ቀድሞ የገባበት ነው። እርሱም እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት ለዘላለም ሊቀ ካህናት ሆኖአል።

6፥8 ዘፍ3፥17፥18፤ ኢሳ5፥6፤27፥4
6፥9 1ቆሮ10፥14
6፥10 ማቴ10፥40-42፤ 1ተሰ1፥3
6፥11 ዕብ3፥6
6፥12 2ተሰ1፥4፤ ዕብ10፥36፤13፥7፤ ያዕ1፥3፤ራእ13፥10፤ 14፥12
6፥13 ዘፍ22፥16፤ ሉቃ1፥73
6፥14 ዘፍ22፥17
6፥15 ዘፍ21፥5
6፥16 ዘፀ22፥1
6፥17 ቍ18፤ መዝ110፥4፤ሮሜ 4፥16፤ዕብ11፥9
6፥18 ዘኍ23፥19፤ ቲቶ1፥2፤ዕብ3፥6
6፥19 ዘሌ16፥2፤ ዕብ9፥2፡3፡7
6፥20 ዕብ2፥17፤ 4፥14፤5፥6
7፥1 ቍ6፤ ዘፍ14፥18-20፤ መዝ76፥2፤ማር5፥7
7፥3 ቍ6፤ማቴ4፥3
7፥4 ዘፍ14፥20፤ ሐሥ2፥29
7፥5 ዘኍ18፥21፡26

## ካህኑ መልከ ጼዴቅ

**7** ይህ መልከ ጼዴቅ የሳሌም ንጉሥና የልዑል እግዚአብሔር ካህን ነበር፤ እርሱም አብርሃም ነገሥታትን ድል አድርጎ ሲመለስ አግኝቶት ባረከው፤ [2]አብርሃምም ከሁሉ ነገር ዓሥራት አውጥቶ ሰጠው። በመጀመ ሪያ ስሙ “የጽድቅ ንጉሥ” ማለት ነው፤ ኋላም ደግሞ “የሳሌም ንጉሥ” ማለትም “የሰላም ንጉሥ ማለት” ነው። [3]አባትና እናት ወይም የትውልድ ሐረግ የለውም፤ ለዘመኑ መጀ መሪያ፣ ለሕይወቱም ፍጻሜ የለውም፤ ነገር ግን እንደ እግዚአብሔር ልጅ ለዘላለም ካህን ሆኖ ይኖራል።

[4]እስቲ እርሱ የቱን ያህል ታላቅ እንደ ሆነ ዐስቡ፤ ርእሰ አበው የሆነው አብር ሃም እንኳ ካገኘው ምርኮ ዓሥራት አው ጥቶ ሰጠው። [5]ክህነት የተሰጣቸው የሌዊ ልጆች ምንም እንኳ ወንድሞቻቸው የአብ ርሃም ዘሮች ቢሆኑም፣ ከሕዝቡ ማለት

---

1ዮሐ 5፥16 ይመ)።

6፥9፤ *ከድነታችሁ ጋር የተያያዘ ታላቅ ነገር እንዳላችሁ እርግጠኞች ነን፤* ምንም እንኳ የመልእክቱ ጸሐፊ፣ ከተደራሲ ዎቹ መካከል አንዳንዶቹ ገና ድነት ያልተከበሉ መሆናቸውን ቢናገርም፣ እግዚአብሔር በመካከላቸው እንደሚሠራ እርግጠኛ ነው። የተለወጠው ሕይወታቸውና የፍቅር ሥራቸው(ቍ 10) በእርግጥም ብዙዎቹ ዳግም ልደት ያገኙ መሆናቸውን ይመሰክራል።

6፥11 *እስከ መጨረሻ፤* በእምነታቸው እስከ መጨረሻ ጸንተው እንዲገኙ የቀረበ ጥሪ ነው፤ ምክንያቱም ድነት እንደ ተቀበሉ የሚያረጋግጡት ጸንተው ሲገኙ ነው። *የተሰጠው ተስፋ፤* 11፥1፤ 2ጴጥ 1፥10 ይመ።

6፥12 *በእምነትና በትዕግሥት የተስፋውን ቃል የሚወርሱትን፤* እነማን እንደሆኑ ምዕ11 ይመ።

6፥13 *እግዚአብሔር ለአብርሃም ተስፋ በሰጠው ጊዜ፤* ዘሩን እንደሚያበዛለት የሰጠውን ተስፋ ያጸናለት በመሐላ ነው፤ ይህም ተስፋው የማይለወጥ መሆኑን ያረጋግጣል (ዘፍ 22፥16-18 ይመ)። በመሠረቱ መሐላ በኀጢያት የወደቁ ሰዎች መለያ ነው፤ ምክንያቱም የሰዎች ቃል ሁልጊዜ የሚታመን አይደለም። እግዚአብሔር የተናገረውን ቃል በመሐላ ሲያጸና ራሱን በወደቁ ሰዎች ደረጃ ዝቅ አድርጎአል፤ በዚህ ዐይነት ፍጹም ታማኝ የሆነውን ቃሉን ይበልጥ ታማኝ አደረገ (ቍ 18 ይመ)።

6፥15 *በትዕግሥት ከጠበቀ በኋላ፤* ለ25 ዓመት ጠብቋል (ዘፍ 12፥3-4፤ 21፥5 ይመ)። *የተሰጠውን ተስፋ አገኘ፤* ልጁ ይስሐቅ ተወለደ ነው (ዘፍ 17፥2፤18፥10፤21፥5)።

6፥18 *በሁለት በማይለወጡ ነገሮች፤* ፍጹም ታማኝ የሆነውን የእግዚአብሔርን የተስፋ ቃልና ተስፋውን የሚያጸና ውን የእግዚአብሔርን መሐላ ነው። *ብርቱ መጽናናት እንድ ናገኝ አድርጎአል፤* የምንጽናናው አብርሃም በተስፋ ብቻ ያየውን (11፥13፤ ዮሐ 8፥56) የተስፋውን ቃል ፍጻሜ ወደኋላ ተመልሰን መመልከት ስለምንችል ነው።

6፥19 *የነፍስ መልሕቅ የሆነ ጽኑና አስተማማኝ፤* መልሕቅ አንድ መርከብ ስፍራዋን ጠብቃ እንድትቆም እንደሚያደርግ ሁሉ፣ በክርስቶስ ያለን ተስፋም የድነታችን ዋስትና ነው። *ከመጋረጃው በስተጀርባ ወዳለው ውስጠኛ መቅደስ፤* የመርከቦች መልሕቅ የሚጣለው ወደ ታች ወደ ባሕሩ ወለል ሲሆን፣ የክር ስቲያኖች መልሕቅ ግን ወደ ላይ ወደ እውነተኛዪቱ ሰማያዊት መቅደስ በመሄድ በራሱ በእግዚአብሔር ላይ ይታሰራል።

6፥20 *እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት ለዘላለም ሊቀ ካህናት፤* የመልእክቱ ጸሐፊ በሰፊው የሚያብራራው ዐቢይ ጭብጥ ነው (ምዕ 7)።

7፥1 *መልከ ጼዴቅ፤* ዘፍ 14፥18-20 እና ማብ ይመ። *ንጉሥና...ካህን፤* መልከ ጼዴቅ ንጉሥም ካህንም መሆኑ ልዩ ትኩረት ተሰጥቶታል፤ ይህም የክርስቶስ ምሳሌ ሆኖ ከቀረበባቸው መንገዶች አንዱ ነው። *የሳሌም፤* ኢየሩሳሌም ማለት ነው (የዘፍ 14፥18 ማብ ይመ)።

7፥2 *የጽድቅ ንጉሥ...የሳሌም ንጉሥ፤* ለመሲሑ የተሰጡ መዓርጋት ናቸው (ኢሳ 9፥6-7፤ ኤር 23፥5-6፤ 33፥15-16 ይመ)።

7፥3 *አባትና...የለውም...ለሕይወቱም ፍጻሜ የለውም፤* በመጀመሪያዎቹ የዘፍጥረት ምዕራፎች ውስጥ ከምናየው ነገር የተለየ ሲሆን፣ በዘፍ 14፥18-20 ላይ ስለ መልከ ጼዴቅ የትውልድ ሐረግም ሆነ የልጅነት ዘመን ወይም ሥራ፣ ስደቱም ሆነ ሞቱ ምንም የጠቀሰ ነገር የለም። በአንዳንድ ወቅት ይኖር የነበረ ሰው ስለመሆኑ ግን ግልጽ ነው፤ የዕብራውያን መልእክት ጸሐፊ (የአይሁድን ትርጓሜ በመከተል) ቅዱሳት መጻሕፍት ስለ መልከ ጼዴቅ የትውልድ ሐረግ ሳይናገሩ በዝምታ ቢያልፉም፣ ያን ዝምታ መሠረት በማድረግ መልከ ጼዴቅ የክርስቶስ ምሳሌ መሆኑን ይናገራል። የመልከ ጼዴቅ ክህነት፣ ክርስቶስ ዘላለ ማዊና ክህነቱም ፍጻሜ እንደሌለው ያሳያል። አንዳንድ ሰዎች መልከ ጼዴቅ ለአብርሃም መታየቱን፣ ክርስቶስ ሥጋ ከመልበሱ በፊት ለሰዎች ይገለጥ ነበር ከሚለው ጋር በማያያዝ፣ ለአብርሃም የተገለጠለት ክርስቶስ ነው የሚል እምነት አላቸው፤ ሆኖም “እንደ እግዚአብሔር ልጅ” የሚለው ማነጻጸሪያ ይህ አባባል ትክክል እንዳልሆነ ያመለክታል።

7፥4 *እስቲ እርሱ የቱን ያህል ታላቅ እንደ ሆነ ዐስቡ፤* ዓሥራት የሚቀበል ዓሥራት ከሚሰጥ ይልቅ እንደሚበልጥ የታወቀ ነው፤ ደግሞም “ትንሹ በትልቁ እንደሚባረክ ግልጽ ነው” (ቍ. 7)። በሁለቱም መንገድ ቢሆን መልከ ጼዴቅ ከአብርሃም ይበልጣል።

ከገዛ ወንድሞቻቸው ዓሥራት እንዲቀበሉ ሕጉ ያዛል። [6]ይህ ግን ትውልዱ ከሌዊ ወገን አይደለም፤ ይሁን እንጂ ከአብርሃም ዓሥራት ተቀበለ፤ የተስፋ ቃል የተቀበለውንም ባረከው። [7]ትንሹ በትልቁ እንደሚባረክ ጥርጥር የለውም። [8]በአንድ በኩል ዓሥራት የሚቀበሉት ሟች ሰዎች ናቸው፤ በሌላ በኩል ግን ሕያው ሆኖ እንደሚኖር የተመሰከረለት ይቀበላል። [9]እንዲያውም ዓሥራት የሚቀበለው ሌዊ፣ ራሱ በአብርሃም በኩል ዓሥራት ከፍሎአል ማለት ይቻላል፤ [10]ምክንያቱም መልከ ጼዴቅ አብርሃምን ባገኘው ጊዜ፣ ሌዊ ገና በአባቱ በአብርሃም አብራክ ነበር።

## ኢየሱስ እንደ መልከ ጼዴቅ

[11]ፍጹምነት የተገኘውና ሕጉ ለሕዝቡ የተሰጠው በሌዊ ክህነት መሠረት ቢሆን ኖሮ፣ እንደ አሮን ሳይሆን እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት ያለው ሌላ ካህን መምጣቱ ለምን አስፈለገ? [12]የክህነት ለውጥ ካለ ሕጉም ሊለወጥ ግድ ነውና። [13]ይህ ሁሉ የተነገረለት እርሱ ከሌላ ነገድ ነው፤ ከዚያም ነገድ በመሠዊያ ያገለገለ ማንም የለም። [14]ጌታችን ከይሁዳ ነገድ እንደመጣ ግልጽ ነውና፤ ሙሴ ስለ ካህናት ሲናገር ይህን ነገድ አስመልክቶ የተናገረው ምንም ነገር የለም። [15]እንደ መልከ ጼዴቅ ያለ ሌላ ካህን ቢነሣ ግን እኛ የተናገርነው ይበልጥ ግልጽ ይሆናል፤ [16]እርሱ ካህን የሆነው በማይጠፋ የሕይወት ኀይል መሠረት እንጂ፣ እንደ ትውልዱ የሕግ ሥርዐት አይደለም፤ [17]እንዲህ ተብሎ ተመስክሮለታል፤

"እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት፣
አንተ ለዘላለም ካህን ነህ።"

7፥6 ዘፍ14፥19:20፤ ሮሜ4፥13
7፥8 ዕብ5፥6፤6፥20
7፥11 ቍ17:8:19፤ ዕብ5፥6፤8፥7፤10፥1
7፥13 ቍ11:14
7፥14 ኢሳ11፥1፤ ማቴ1፥3፤2፥6፤ ሉቃ3፥33፤ራእ5፥5
7፥17 ቍ21፤ መዝ110፥4፤ዕብ5፥6
7፥18 ሮሜ8፥3
7፥19 ቍ11:25፤ ሮሜ3፥20፤ 7፥7:8፤ገላ3፥21፤ ዕብ3፥6፤4፥16፤ 9፥9፤10፥1:ዕ22፤ያዕ4፥8
7፥21 ዘኍ23፥19፤ 1ሳሙ15፥29፤መዝ1 10፥4፤ሚል3፥6፤ ሮሜ11፥29፤ዕብ5፥6
7፥22 ሉቃ22፥20
7፥24 ቍ28
7፥25 ቍ19፤ ሮሜ8፥34፤11፥14
7፥26 2ቆሮ5፥21፤ ዕብ2፥17፤4፥14
7፥27 ሮሜ6፥10፤ ኤፌ5፥2፤ዕብ5፥1: 3፤9፥12:14: 26:28፤10፥10፤ 1ጴጥ3፥18
7፥28 ዕብ1፥2፤ 2፥10፤5፥2

[18]የቀድሞው ትእዛዝ ደካማና የማይጠቅም በመሆኑ ተሽሮአል፤ [19]ሕጉ ማንንም ፍጹም ሊያደርግ ስለማይችል ወደ እግዚአብሔር የምንቀርብበት የተሻለ ተስፋ መጥቶአል።

[20]ይህ ያለ መሐላ አልሆነም፤ ሌሎች ካህናት የሆኑት ያለ መሐላ ነው፤ [21]እርሱ ግን ካህን የሆነው በመሐላ ነው፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር እንዲህ ብሎ ተናግሮለታል፤

"ጌታ ማለ፤
ሐሳቡንም አይለውጥም፤
'አንተ ለዘላለም ካህን ነህ።' "

[22]ከዚህ መሐላ የተነሣ፣ ኢየሱስ ለተሻለ ኪዳን ዋስ ሆኖአል።

[23]በአገልግሎታቸው እንዳይቀጥሉ ሞት ስለ ከለከላቸው፣ የቀድሞዎቹ ካህናት ቍጥራቸው ብዙ ነበር፤ [24]ኢየሱስ ግን ለዘላለም የሚኖር በመሆኑ፣ ክህነቱ የማይሻር ነው። [25]ስለዚህ ስለ እነርሱ እየማለደ ሁልጊዜ በሕይወት ስለሚኖር፣ በእርሱ በኩል ወደ እግዚአብሔር የሚመጡትን ፈጽሞ[ሀ] ሊያድናቸው ይችላል።

[26]እንግዲህ ለእኛ የሚያስፈልገን፣ ቅዱስ፣ ነቀፋ የሌለበት፣ ንጹሕ፣ ከኀጢአተኞች የተለየና ከሰማያት በላይ የከበረ እንደዚህ ያለ ሊቀ ካህናት ነው። [27]እርሱም እንደ ሌሎቹ ሊቃነ ካህናት፣ መጀመሪያ ስለራሱ ኀጢአት ከዚያም ስለ ሕዝቡ ኀጢአት በየቀኑ መሥዋዕት ማቅረብ አያስፈልገውም፤ ራሱን በሰጠ ጊዜ፣ ስለ ኀጢአታቸው ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ መሥዋዕት አቅርቦአልና። [28]ሕጉ ደካማ የሆኑትን ሰዎች ሊቃነ ካህናት አድርጎ ይሾማልና፤ ከሕግ በኋላ

[ሀ]25 ወይም *ለዘላለም*

7፥11 ***መሠረት ቢሆን፡*** በሌዋውያን ክህነት መሠረት ነው። ***ሕጉ ... የተሰጠው፡*** የሙሴ ሕግና ክህነት አብረው የሚሄዱ ናቸው። ሰዎች ሁሉ ኀጢአተኞች በመሆናቸው ከሕግ ኵነኔ ሥር ናቸው፤ ስለዚህ በእነርሱና በእግዚአብሔር መካከል ሆኖ የሚ ማልድ ሥርዐተ ክህነት የግድ ያስፈልጋቸዋል። ***እንደ አሮን ሳይሆን እንደ መልከ ጼዴቅ ሹመት፡*** የአሮን (የሌዋውያኑ) ክህነት ፍጹም አለመሆኑን፣ ባንጻሩም የመልከ ጼዴቅ ግን ፍጹም እንደሆነ ያመለክታል። ለዘላለም ካህን የሚሆነው እንደሚመጣ የተነገረው (መዝ 110፥10) የሌዋውያኑ ክህነት አገልግሎት በመስጠት ላይ እያለ ነው፤ ይህም አሁን ያለው ሥርዐተ ክህነት ወደ ፊት በሚመጣው የተሻለ ክህነት እንደሚተካ ያሳያል።

7፥16 ***ካህን የሆነው...እንደ ትውልዱ የሕግ ሥርዐት አይደለም፡*** በሙሴ ሕግ መሠረት በክህነት ማገልገል የሚችሉት ከሌዊ ወገን የሆኑ ብቻ ናቸው (ዘዳ 18፥1)፤ ኢየሱስ ግን የመጣው የክህነት አገልግሎት ካልተሰጠው ከይሁዳ ነገድ ነው (ቍ 14-15)። ***በማይጠፋ የሕይወት ኀይል፡*** በመዝ 110፥4 መሠረት በመልከ ጼዴቅ ሹመት ሥርዐት የሚመጣ ካህን "የዘላለም ካህን" ነው።

7፥18 ***የቀድሞው ትእዛዝ ደካማና የማይጠቅም በመሆኑ፡*** ሕጉ ቅዱስና መልካም ነው (ሮሜ 7፥12)፤ ይሁን እንጂ ሕጉን በመተላለፍ ኀጢአት የሚሠሩትን ሊያጸድቃቸው ወይም ሕጉ የሚጠይቀውን ሁሉ ለመፈጸም የሚያስችል ኀይል ሊሰጣቸው አይችልም (ቍ. 19)።

*1፥19፤* ሕጉ ወደ ፊት ለሚመጣው የሚያዘጋጅ ብቻ እንጂ (ገላ 3፥23-25 ይመ) ፍጹም ሊያደርግ አይችልም (ማቴ 5፥17 ይመ)። ***የተሻለ ተስፋ፤*** አዲሱ ኪዳን የተሻለ ነው፤ ምክንያቱም ያገኘነው ቤዛነት ፍጹምና ወደ እግዚአብሔርም ፊት ሊያቀርበን የሚችል መሆኑን ያረጋግጥልናል። የቈላ 1፥5 ማብ ይመ።

*7፥20፤* የሌዋውያኑ ክህነት ሲመሠረት እግዚአብሔር አል ማለም። በመዝ110 ላይ ቃል የተገባው ክህነት በመሐላ የጸና በመሆኑ እጅግ የላቀ ነው።

7፥22 ***ለተሻለ ኪዳን፡*** ምዕ8-10 ይመ።

7፥23 ***በአገልግሎታቸው እንዳይቀጥሉ ሞት ስለ ከለከላቸው፤*** የሌዋውያኑ ሥርዐተ ክህነት ፍጹም እንዳልሆነ የሚያሳይ ተጨማሪ ማስረጃ ነው።

7፥25 ***ፈጽሞ፡*** ፍጹምነትና ሙሉነት የሚለውን ሐሳብ ሊይዝ ይችላል፤ አማራጭ ትርጕሙን ይመ። ኢየሱስ ለዘላለም ፍጹም ሊቀ ካህናት ነው፤ በመሆኑም ፈጽሞና ሁልጊዜ ሊያድነን ይችላል። ***እየማለደ ሁልጊዜ በሕይወት ስለሚኖር፡*** ሕዝቡ ያለ ካህን የሚሆንበት ጊዜ አይኖርም (ዮሐ 17፤ 1ዮሐ 2፥1 ይመ)።

7፥26 ***የሚያስፈልገን፡*** ከኀጢአትና ኀጢአት ከሚያስከትለውም ቅጣት ሊታደገን የሚችል ነው።

7፥27 ***በየቀኑ፡*** ዓመቱን በሙሉ ያለማቋረጥ የሚቀርበውን መሥዋዕት የሚያመለክት ሲሆን (ዘፀ 29፥36-42)፣ ይህም መሥዋዕቱ በማያዳግም ሁኔታ ለኀጢአት መፍትሔ ሊሰጥ እንደማይችል አንዱ ማስረጃ ነው። ***መጀመሪያ ስለ ራሱ ኀጢአት፡*** ኀጢአት የሌለበት ስለ ሆነ፣ ስለ ራሱ መሥዋዕት ማቅረብ አያስፈልገውም፤ ስለ ዚህም የክርስቶስ ክህነት የላቀ ነው። ***ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ፤*** በዕብራውያን መልእክት ውስጥ ቍልፍ ሐረግ ነው (9፥12፤26፤ 10፥2፤10 ይመ)። ሌዋውያን ካህናት በየዕለቱ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ማቅረብ ነበረባቸው፤ ኢየሱስ ግን ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ራሱን መሥዋዕት አድርጎ አቀረበ። ***ራሱን በሰጠ ጊዜ፤*** ሌዋውያን ካህናት መሥዋዕት አድርገው የሚያቀርቡት እንስሳትን ብቻ ሲሆን፣ የእኛ ሊቀ ካህን ግን ራሱን መሥዋዕት አድርጎ አቀረበ፤ በዚህ ዐይነት ፍጹም ምትክ ሆነን።

7፥28 ***ደካማ የሆኑትን ሰዎች፤*** ደካማ የሆኑት (1) ሟችና ከዚህም የተነሣ ዘላለማዊነት የሌላቸው በመሆኑ ቍ 23፤ (2)

የመጣው መሐላ ግን ለዘላለም ፍጹም የሆነውን ልጅ ሾሞአል።

## የአዲስ ኪዳን ሊቀ ካህናት

**8** እንግዲህ የምንናገረው ዋናው ነገር ይህ ነው፤ በሰማያት በግርማው ዙፋን ቀኝ የተቀመጠ እንዲህ ያለ ሊቀ ካህናት አለን፤ [2]እርሱም በሰው ሳይሆን በጌታ በተተከለችው፣ እውነተኛ ድንኳን በሆነችው ቤተ መቅደስ አገልጋይ ነው።

[3]እያንዳንዱ ሊቀ ካህናት የሚሾመው መባንና መሥዋዕትን ለማቅረብ ነው፤ ስለ ዚህ ይኸኛውም ካህን የግድ የሚያቀርበው ነገር ያስፈልገዋል። [4]እርሱ በምድር ቢኖር ኖሮ ካህን ባልሆነም ነበር፤ ምክንያቱም በሕግ በታዘዘው መሠረት መባን የሚያቀርቡ ሰዎች አሉ። [5]እነርሱ ያገለገሉት በሰማይ ላለችው መቅደስ ምሳሌና ጥላ በሆነችው ውስጥ ነው፤ ሙሴ ድንኳኒቱን ለመሥራት በተነሣ ጊዜ፣ "በተራራው ላይ በተገለጠልህ ምሳሌ መሠረት ሁሉን ነገር እንድታደርግ ተጠንቀቅ" የሚል ትእዛዝ የተሰጠው በዚህ ምክንያት ነበር። [6]ነገር ግን ኢየሱስ መካከለኛ የሆነበት ኪዳን ከቀድሞው እንደሚበልጥ ሁሉ፣ የተቀበለውም አገልግሎት ከእነርሱ አገልግሎት ይበልጣል፤ ይህም የተመሠረተው በተሻለ የተስፋ ቃል ላይ ነው።

[7]የመጀመሪያው ኪዳን ምንም ጒድለት ባይገኝበት ኖሮ፣ ለሁለተኛው ስፍራ ባልተፈለገም ነበር። [8]ነገር ግን እግዚአብሔር በሕዝቡ ላይ ጒድለት በማግኘቱ እንዲህ ይላቸዋል†፤

"ከእስራኤል ቤት ጋር፣
ከይሁዳም ቤት ጋር፣
አዲስ ኪዳን የምገባበት፣
ጊዜ ይመጣል፤
ይላል ጌታ።
[9]ይህም እነርሱን ከግብፅ ምድር ለማውጣት
እጃቸውን በያዝሁ ጊዜ፣
ከቀድሞ አባቶቻቸው ጋር እንደ ገባሁት ኪዳን
አይደለም፤
ምክንያቱም እነርሱ በኪዳኔ አልጸኑም፤
እኔም ከእነርሱ ዘወር አልሁ፤
ይላል ጌታ።
[10]ከዚያን ጊዜ በኋላ፣
ከእስራኤል ቤት ጋር የምገባው ኪዳን
ይህ ነው፤
ይላል ጌታ፤
ሕጌን በአእምሮአቸው አኖራለሁ፤
በልባቸውም እጽፈዋለሁ።
እኔ አምላካቸው እሆናለሁ፤
እነርሱም ሕዝቤ ይሆናሉ።
[11]ከእንግዲህ ማንም ሰው ጐረቤቱን ወይም
ወንድሙን፣
'ጌታን ዕወቅ' ብሎ አያስተምርም፤
ምክንያቱም ከታናሹ ጀምሮ እስከ
ታላቁ ድረስ፣
ሁሉም ያውቁኛል።
[12]በደላቸውን ይቅር እላለሁ፤ ኀጢአታቸውን
ከእንግዲህ አላስብም፤

[13]ይህን ኪዳን፣ "አዲስ" በማለቱ የፊተኛውን ኪዳን አሮጌ አድርጎታል፤ ስለዚህ ያረጀ ያፈጀው የሚጠፋበት ጊዜ ተቃርቦአል።

8፥1 ማር16፥19፤ ዕብ2፥17፤4፥14
8፥2 ዕብ9፥11፡24
8፥3 ዕብ2፥17፤ 5፥1፡9፥9፡14
8፥4 ዕብ5፥1፤9፥9
8፥5 ዘፀ25፥40፤ ቈላ2፥17፤ዕብ9፥23፤ 10፥1፤11፥7፤12፥25
8፥6 ቊ8፡13፤ ሉቃ22፥20፤፻3፥20
8፥7 ዕብ7፥11፡ 18፤10፥1
8፥8 ቊ6፡13፤ ሉቃ22፥20
8፥9 ዘፀ19፥5፡6፤ 20፥1-17
8፥10 ሕዝ11፥20፤ ዘካ8፥8፤ሮሜ 11፥27፤2ቆሮ3፥3፤ ዕብ10፥16
8፥11 ኢሳ54፥13፤ ዮሐ6፥45
8፥12 ኤር31፥31-34፤ ዕብ10፥17
8፥13 ቊ6፡8፤ ሉቃ22፥20፤2ቆሮ5፥17

†8 አንዳንድ የጥንት ቅጆች *ጒድለት በማግኘቱ ለሕዝቡ እንዲህ ይላቸዋል*

---

ኀጢአተኞች በመሆናቸውና ቊ. 27፤ (3) ማቅረብ የሚችሉት መሥዋዕት እንስሳትን ብቻ በመሆኑና እንሳሳት ደግሞ በእግዚአብሔር አምሳል ለተፈጠረ ሰው፣ ትክክለኛ ምትክ መሆን ስለማይችሉ ነው (ዘፍ 1፥26-28 እና ማብ ይመ)። *ለዘላለም ፍጹም የሆነውን፤* ክርስቶስ ፍጹም ሊሆን የቻለው በኀጢአት ሳይሸነፍ ፈተናን በመቀበሉ ነው (የ2፥10፤5፥8 ማብ ይመ)። ይልቁንም አባቱን ፍጹም በመታዘዙ፣ ዘላለማዊ ፍጽምናን መሠረተ።

*8፥1-10፥39፤* የዚህ ክፍል ዐቢይ ሀሳብ የሠረጸው በኤር 31፥31-34 ከተሰጠው ትንታኔ ሲሆን፣ ክርስቶስ "ለተሻለ ኪዳን" መካከለኛ መሆኑን አጒልቶ የሚያሳይ ነው (7፥22)።

8፥1፤ የ1፥2-3 ማብ ይመ። *በሰማያት በግርማው፤* አይሁድ እግዚአብሔርን ለማመልከት የሚጠቀሙበት አባባል ነው (1፥3 ይመ)።

8፥2 *እውነተኛ ድንኳን፤* ሙሴ ከተከላት ፍጹምና ዘላለማዊ ካልሆነችው እንዲሁም ለሰማያዊቷ ድንኳን ምሳሌ ከሆነችው ጋር ሲነጻጸር ነው። *በሰው ሳይሆን በጌታ በተተከለችው፤* እግዚአብሔር የሠራት ሰማያዊቷ ድንኳን ሙሴ ከሠራትና ሊቀ ካህኑ በዓመት አንድ ጊዜ የማስተስረያውን ደም ይዞ ከሚገባበት ቅድስትና ቅድስተ ቅዱሳን ጋር ትመሳሰላለች (ዘሌ 16፥13-15፤ 34)። ታላቁ ሊቀ ካህናችን ግን አማላጃችን ሆኖ በሰማያዊቷ መቅደስ ውስጥ ለዘላለም ይኖራል (7፥25)።

8፥3 *መባንና መሥዋዕትን፤* የ5፥1 ማብ ይመ።

8፥4 *ካህን ባልሆነም ነበር፤* ክርስቶስ በሥጋ የተወለደው ከይሁዳ ነገድ ነው፤ የይሁዳ ነገድ ደግሞ ከካህናት ወገን አይደለም (7፥12-14 ይመ)። *መባን የሚያቀርቡ ሰዎች፤* ከሌዊ ነገድ የሆኑ ናቸው እዚህም ላይ ሆነ በመልእክቱ ውስጥ በሌላ ስፍራ የሚያቀርቡ የሚለው የአሁን ጊዜ ግስ የሚያመለክተው በኢየሩሳሌም የሚገኘው ቤተ መቅደስ እንደቆመ ነው። እንግዲህ ይህ መልእክት የተጻፈው ቤተ መቅደሱ በ70 ዓ.ም. ላይ ከመፍረሱ በፊት ነው ማለት ነው (በመልእክት "መግቢያ" ላይ "መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜና ቦታ" የሚለውን ይመ)።

8፥5 *በሰማይ ላለችው መቅደስ ምሳሌና ጥላ፤* ሊቀ ካህናችን ክርስቶስ የራሱን ደም ይዞ የገባው ወደ እውነተኛዪቱና እግዚአብሔር ወደሚኖርባት መቅደስ ነው (9፥11-12 ይመ)። *በተገለጠልህ ምሳሌ መሠረት ሁሉን ነገር እንድታደርግ፤* ድንኳኒቱም ሆነች የአገልግሎቱ ሥርዐት የቀረቡት ኀጢአተኞች ቅዱስ ወደሆነው አምላክ በመቅረብ የሚችሉት በዚህ መንገድ ብቻ መሆኑን በምሳሌ ለመግለጽ ነው።

8፥6 *ኢየሱስ መካከለኛ የሆነበት ኪዳን ከቀድሞው እንደሚበልጥ ሁሉ፤* 9፥15፤ 12፥24፤ 1ጢሞ 2፥5 ይመ። ኢየሱስ መካከለኛ የሆነበት አዲሱ ኪዳን (ቊ. 8-12፤ ኤር 31፥31-34 ይመ) እግዚአብሔር፣ በሲና ተራራ ላይ በሙሴ አማካይነት ከሰጠው ኪዳን ይበልጣል (ዘፀ 24፥7-8 ይመ)። *የተመሠረተው በተሻለ የተስፋ ቃል ላይ ነው፤* ቊ 10-12 ይመ።

8፥7 *የመጀመሪያው ኪዳን ምንም ጒድለት ባይገኝበት ኖሮ፤* እዚህ ላይ የቀረበው ሐሳብ በ7፥11 ላይ ካለው ጋር ተመሳሳይነት አለው፤ ይኸውም የሌዋውያኑን ሥርዐተ ክህነት እንደሚያንስ በግልጽ ታይቶአል፤ ምክንያቱም በመልከ ጼዴቅ ሥርዐት በመጣው ክህነት ተተክቶአል። በተመሳሳይ ሁኔታ ለሙሴ የተሰጠው ኪዳን ጒድለት ባይኖረው ኖሮ፣ በአዲስ ኪዳን መተካት ባላስፈለገም ነበር። እንደ እውነቱ ከሆነ ግን በሙሴ በኩል የመጣው ኪዳን "ጒድለት" የለበትም። የ7፥17 ይመ።

*8፥8-12፤* ከኤርምያስ 31፥31-34 ላይ የተወሰደ ትንቢታዊ ዐዋጅና የአዲሱ ኪዳን ትርጓሜ ነው፤ ይህም ኪዳን በሙሴ በኩል ከመጣው ኪዳን ፍጽም ልዩ ነው (ቊ 9)። ከዚህ ኪዳን የሚገኙት ዐበይት ጥቅሞች፦ (1) የእግዚአብሔር ሕግ የኀሊና መርሕ በመሆን (ቊ. 10)፣ ሕዝቡ ፈቃዱን በመፈጸም ደስ እንዲላቸው ያደርጋል (ከሕዝ 36፥26-27፤ ከሮሜ 8፥2-4 ጋር ያነጻጽሩ)፤ (2) በእግዚአብሔርና በሕዝቡ መካከል ጥብቅ ግንኙነት እንዲኖር ያደርጋል (ቊ 10)፤ (3) እግዚአብሔርን ያለማወቅ ኀጢአት ለዘላለም ይወገዳል (ቊ 11)፤ እንዲሁም (4) የኀጢአት ይቅርታ ከዘላለም እስከ ዘላለም የሚኖር እውነት ይሆናል (ቊ 12)።

8፥13 *ያረጀ ያፈጀው፤* የአዲሱ ኪዳን መታወጅ የቀድሞው ኪዳን ጊዜያዊ መሆኑን ያረጋግጣል። በመሆኑም ወደ

## በምድራዊው ድንኳን የሚደረግ አምልኮ

**9** የመጀመሪያው ኪዳን የአምልኮ ሥርዐትና ምድራዊ መቅደስ ነበረው:: [2]ድንኳን ተተክሎ ነበር፤ በመጀመሪያው ክፍል መቅረዙ፣ ጠረጴዛውና የመሥዋዕቱ ኅብስት ነበረበት፤ ይህም ስፍራ ቅድስት ይባላል:: [3]ከሁለተኛው መጋረጃ በስተኋላ ቅድስተ ቅዱሳን የተባለ ክፍል ነበር፤ [4]በዚያም ውስጥ የወርቅ ማዕጠንትና በወርቅ የተለበጠው የኪዳኑ ታቦት ነበሩ፤ ይህም ታቦት መና ያለበትን የወርቅ መሶብ፣ የለመለመችውን የአሮንን በትርና ኪዳኑ የተጻፈበትን ጽላት ይዞአል:: [5]በታቦቱም ላይ የስርየት መክደኛውን[፣] የሚጋርዱ የክብር ኪሩቤል ነበሩ፤ አሁን ግን ስለ እነዚህ ነገሮች በዝርዝር መናገር አንችልም::

[6]ሁሉም በዚህ መልክ ከተዘጋጀ በኋላ፣ ካህናት አገልግሎታቸውን ለመፈጸም ዘወትር ወደ ድንኳኒቱ መጀመሪያ ክፍል ይገባሉ:: [7]ነገር ግን ወደ ውስጠኛው ክፍል የሚገባው ሊቀ ካህናቱ ብቻ ነበር፤ የሚገባውም በዓመት አንድ ጊዜ ብቻ ሲሆን፣ ስለ ራሱ ኀጢአትና ሕዝቡ ባለማወቅ ስላደረገው ኀጢአት የሚያቀርበውን ደም ሳይዝ ከቶ አይገባም ነበር:: [8]የመጀመሪያዪቱ ድንኳን ቆማ እስካለች ድረስ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን የሚወስደው መንገድ ገና እንዳልተገለጠ መንፈስ ቅዱስ ያሳያል:: [9]ይህም ለአሁኑ ዘመን ምሳሌ ሲሆን፣ የሚቀርቡት መባና መሥዋዕት የሚያመልከውን ሰው ኅሊና ፍጹም ሊያደርጉ አልቻሉም:: [10]እነዚህ ሁሉ አዲሱ ሥርዐት እስኪመጣ ድረስ የሚደረጉ የምግብና የመጠጥ እንዲሁም የተለያዩ የመጠንጸት ሥርዐቶች ብቻ ናቸው::

## የክርስቶስ ደም

[11]ክርስቶስ አሁን ስላሉት[ᵓ] መልካም ነገሮች ሊቀ ካህናት ሆኖ በመጣ ጊዜ በሰው እጅ ወዳልተሠራችው፣ ከዚህ ፍጥረት ወዳልሆነችው ታላቅና ፍጹም ድንኳን ገባ:: [12]የገባውም የፍየልንና የጥጃዎችን ደም ይዞ አይደለም፤ ነገር ግን የዘላለም ቤዛነት ሊያስገኝ የራሱን ደም ይዞ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ገባ:: [13]የውጭ አካላቸው ይነጻ ዘንድ በረከሱ ሰዎች ላይ የሚረጨው የፍየሎችና የኮርማዎች ደም እንዲሁም የፍየሎችና የጊደር ዐመድ የሚቀድሳቸው ከሆነ፣ [14]በዘላለም መንፈስ አማካይነት ራሱን ነውር አልባ መሥዋዕት አድርጎ ለእግዚአብሔር ያቀረበው የክርስቶስ ደም ሕያው እግዚአብሔርን እንድናመልክ ኅሊናችንን ከምውት ሥራ[ʾ] እንዴት ይበልጥ ያነጻ ይሆን!

[15]ስለዚህም የተጠሩት፣ ተስፋ የተሰጠውን የዘላለም ርስት እንዲቀበሉ ክርስቶስ የአዲስ ኪዳን መካከለኛ ነው፤ በመጀመሪያው ኪዳን ሥር በነበሩበት ጊዜ ከሠሩት

9፥1 ዘፀ25፥8
9፥2 ዘፀ25፥8:9: 23-29:30:31-39፤ 26፥33:34፤ዘሌ24፥5-8
9፥3 ዘፀ26፥31-33
9፥4 ዘፀ16፥32: 33፤25፥10-22፤ 30፥1-5፤31፥18፤ 32፥15፤ዘኍ17፥10
9፥5 ዘፀ25፥17-19፤ 20-22፤26፥34
9፥6 ዘኍ28፥3
9፥7 ቀኍ2:3፤ ዘሌ16፥11-19:34፤ ዕብ5፥2:3
9፥8 ዮሐ14፥6፤ ዕብ3፥7፤10፥19:20
9፥9 ዕብ5፥1፤7፥19፤ 8፥3፤10፥1
9፥10 ዘሌ11፥2-23: 25:28:40፤ዘኍ6፥3፤ ቈላ2፥16፤ ዕብ2፥17፤8፥2፤10፥1
9፥11 ቀኍ24፤ ዮሐ2፥19:24:26:28፤ ዘሌ16፥6:15፤ ሮሜ3፥25፤ ዕብ7፥27፤10፥4
9፥13 ዘኍ19፥9: 17:18፤ዕብ10፥4
9፥14 መዝ51፥2፤ 65፥3፤ኤር33፥8፤ ዘካ13፥1፤ማቴ16፥16፤ ኤፌ5፥2፤ ቲቶ2፥14፤ 1ጴጥ3፥18፤ዕብ6፥1፤ 10፥2:22
9፥15 ሉቃ22፥20፤ ሐሥ20፥32፤ሮሜ 8፥28፤11፥29፤ገላ3፥20፤ ዕብ6፥15፤7፥22፤ 10፥36

*[፣]*5 ወይም *የማስተሰረያውን መክደኛ*
*[ᵓ]*11 አንዳንድ የጥንት ቅጆች *ሊመጡ ስላሉት* ይላሉ::
*[ʾ]*14 ወይም *ከከንቱ የዘወትር ሥርዐቶች*

ቀደመው ሥርዐት መመለስ ማለት ወዳረጀው ወይም ከጥቅም ውጭ ወደ ሆነው መመለስ ማለት ነው::

9፥2 *ድንኳን ተተክሎ ነበር*፤ በሙሴ የተሠራውን ድንኳን ነው:: *መቅረዙ፤* ከቅጥቅጥ ወርቅ የተሠራና በቅድስት ውስጥ በተቀደሰው ቦታ በስተደቡብ የሚቀመጥና (ዘጸ 40፥24)፣ በየምሽቱ ያለ ማቋረጥ የሚበሩ ሰባት መብራቶች ያሉት ነው (ዘጸ 25፥31-40):: *ጠረጴዛውና የመሥዋዕቱ ኅብስት*፤ ከግራር እንጨት የተሠራና በወርቅ የተለበጠ፣ በቅድስት ውስጥ በስተሰሜን የሚቀመጥ ነው (ዘጸ 40፥22):: በኅብስት ማስቀመጫው ጠረጴዛ ላይ በሁለት ረድፍ የተደረደሩ ስድስት ስድስት ኅብስቶች ይገኛሉ (ዘሌ 24፥5-6)::

9፥4 *የወርቅ ማዕጠንትና ... ነበሩ፤* ማዕጠንቱ የተቀመጠው በቅድስት ውስጥ ቢሆንም፣ የመልእክቱ ጸሓፊ ግን በቅድስተ ቅዱሳኑ ውስጥ እንደሚገኝ አድርጎ ይገልጻል:: እንዲህ ያደረገው ቅድስተ ቅዱሳኑ ከኪዳኑ ታቦት ጋር ያለውን የቅርብ ግንኙነት ለማሳየት ነው (ከዘጸ 40፥5፤ 1ነገ 6፥22 ጋር ያነጻጽሩ):: ሊቀ ካህኑ በስርየት ቀን ከማዕጠንቱ ላይ ዕጣን በመውሰድና ለኀጢአት ማስተስረያ የሚሆነውን ደም በመያዝ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ይገባል (ዘሌ 16፥12-14):: *የኪዳኑ ታቦት*፤ ከውስጥም ከግራር እንጨት ተሠርቶ ከውስጥና ከውጭ በወርቅ የተለበጠ ሣጥን ነው (ዘጸ 25፥10-16):: *መና ... በትርና ... ጽላት*፤ የዘፀ 16፥33-34 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዘኍ 17፥8-10 ይመ::

9፥5 *የክብር ኪሩቤል፤* ከንጹሕ ወርቅ የሚሠሩ እያንዳንዳቸው ሁለት ክንፍ ያላቸው ምስሎችና በስርየት መክደኛው ላይ ከዳርና ዳር ትይዩ የሚቆሙ ናቸው:: የእግዚአብሔር ክብር የሚገለጠው በሁለቱ መካከል ነበር (ዘጸ 25፥17-22፤ ዘሌ 16፥2፤ ዘኍ 7፥89):: *የስርየት መክደኛውን፤* ከንጹሕ ወርቅ የተሠራና፣ የኪዳኑን ታቦት ሙሉ በሙሉ የሚሸፍን ዝርግ ግጣም ነው፤ ሊቀ ካህኑ በስርየት ቀን የኀጢአት ማስተስረያው ደም የሚረጨው በዚህ ግጣም ላይ ነው (ዘሌ 16፥14-15)::

9፥7 *በዓመት አንድ ጊዜ ብቻ*፤ በስርየት ቀን (ዮም ኪፑር) በሰባተኛው ወር በዐሥረኛው ቀን ማለት ነው (ዘሌ 16፥29፤34):: በዚህ ቀን ስለሚፈጸመው ሥርዐት ዘሌ 16 እና ማብራሪያዎቹን ይመ::

9፥8 *የመጀመሪያዪቱ ድንኳን ቆማ እስካለች ድረስ፤* የሙሴ ሥርዐት ይኸውም፣ ፍጹም ያልሆነው ክህነትና መሥዋዕት እስካለ ድረስ ማለት ነው (8፥7-8፤13)::

9፥9 *ለአሁኑ ዘመን ምሳሌ፤* ምንም እንኳ የሙሴ ድንኳን በሌላ የተተካ ቢሆንም፣ በሥርዐቱ ውስጥ የሚገኙት ትእምርቶች (ምሳሌዎች) ግን፣ አሁንም ትምህርት የሚሰጡና ወደ አሮጌው ሥርዐት መመለስ ከንቱ መሆኑን የሚያስገነዝቡ ናቸው፤ አሮጌው ሥርዐት ኀጢአትን ፈጽሞ ሊያስወግድ አይችልምና:: *መባና መሥዋዕት*፤ የ5፥1 ማብ ይመ::

9፥10 *አዲሱ ሥርዐት*፤ አዲሱን ኪዳንና ከእርሱም ጋር የመጡትን አዲሱን ክህነት፣ አዲሱን ቤተ መቅደስና አዲሱን ሥርዐት ነው፤ ይህ ሁሉ የተገኘው በክርስቶስ ነው::

9፥11 *ከዚህ ፍጥረት ወዳልሆነችው*፤ ምድራዊ ድንኳን ሳትሆን፣ እግዚአብሔር የሚኖርባት ሰማያዊቷ መቅደስ ናት (ቀኍ 24፤8፥2)::

9፥12 *ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ገባ*፤ ሌዋውያን ሊቀ ካህናት በየዓመቱ በመደጋገም እንደሚያደርጉት አይደለም፤ የክርስቶስ መሥዋዕትነት ፍጹም ነው፤ ምክንያቱም የሚሠራና በመደጋገም ሊቀርብ የማያስፈልገው ነው:: ዘላለማዊ ቤዛነት ከተቀዳጀ በኋላ፣ ክርስቶስ ወደ እውነተኛዪቱ ሰማያዊ ቤተ መቅደስ ዐረገ::

9፥13 *የፍየሎችና የኮርማዎች ደም*፤ በስርየት ቀን የሚቀርብ የእነዚህ እንስሳት ደም ነው:: *የጊደር ዐመድ*፤ በዘኍ 19 ላይ እንደተጠቀሰው የሞተ ሰው የነኩ ሰዎች በሥርዐቱ መሠረት ስለሚረከሱ የጊደር ዐመድ ይረጫሉ:: *የውጭ አካላቸው*፤ የሚረጩት ውጫዊ አካላቸውን ብቻ ስለ ሆነ፣ እንዲህ ዐይነቱ ሥርዐት ሰውን ከኀጢአቱ አያነጻውም::

9፥14 *ራሱን ... መሥዋዕት አድርጎ ... ያቀረበው*፤ መሥዋዕቱን ያቀረበውም ሆነ መሥዋዕቱ እርሱ ራሱ ነው:: *ነውር አልባ፤* ላይ ላዩን ብቻ ሳይሆን፣ መላ እሱነቱ እንከን የሌለበት መሆኑን ለመግለጽ ነው:: *ኅሊናችንን ... ያነጻ ይሆን!* የኀጢአትን ርኵሰት፣ ከእኛነታችን ውስጥ ጨርሶ ያስወግዳል::

9፥15 *መካከለኛ፤* 8፥6 እና ማብራሪያውን ይመ፤ ማስታወሻውን፤ እንዲሁም 12፥24፤ 1ጢሞ 2፥5 ይመ:: *የአዲስ ኪዳን፤* 7፥22፤8፥6:13 ይመ:: *ተስፋ የተሰጠውን የዘላለም ርስት*፤ ከኤርምያስ ትንቢት (31፥31-34) ላይ ተወስዶ በ8፥8-21 ላይ

ኀጢአት ነጻ ለማውጣት ቤዛ ሆኖ ሞቶ አልና::

[16]ኑዛዜ[ገ] በሚኖርበት ጊዜ የተናዛዡን ሞት ማረጋገጥ ግድ ነው፤ [17]ምክንያቱም ኑዛዜው የሚጸናው ሰውዬው ሲሞት ብቻ ነው፤ ነገር ግን ተናዛዡ በሕይወት እስካለ ድረስ ኑዛዜው ዋጋ አይኖረውም:: [18]ስለዚህ የመጀመሪያው ኪዳን እንኳ ያለ ደም የጸና አልነበረም:: [19]ሙሴ እያንዳንዱን የሕግ ትእዛዝ ለሕዝቡ ሁሉ ከተናገረ በኋላ የጥጆችን ደም ከውሃ፣ ከቀይ የበግ ጠጕርና ከሂሶጵ ጋር ወስዶ፣ በመጽሐፉና በሕዝቡ ላይ ረጨው፤ [20]እንዲህም አለ፤ "እንድትጠብቁት እግዚአብሔር ያዘዛችሁ የኪዳኑ ደም ይህ ነው::" [21]እንዲሁም ድንኳኒቱንና ማገልገያ ዕቃውን ሁሉ በደም ረጨው:: [22]በእርግጥ ከጥቂት ነገሮች በስተቀር ሁሉም ነገር በደም መንጻት እንዳለበት ሕጉ ያዛል፤ ደም ሳይፈስ ስርየት የለምና::

[23]እንግዲህ የሰማያዊው ነገሮች ምሳሌ የሆኑት በእነዚህ ነገሮች ሊነጹ ግድ ነበር፤ በሰማይ ያሉት ነገሮች ግን ከዚህ በሚበልጥ መሥዋዕት ይነጻሉ:: [24]ክርስቶስ የእውነተኛዪቱ ድንኳን ምሳሌ ወደ ሆነችውና በሰው እጅ ወደ ተሠራችው መቅደስ አልገባም፤ ነገር ግን አሁን ስለ እኛ በእግዚአብሔር ፊት ለመታየት፣ ወደ እርሷ ወደ ሰማይ ገባ:: [25]ሊቀ ካህናት የራሱ ያልሆነውን ደም ይዞ በየዓመቱ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን እንደሚገባ፣ ክርስቶስ ራሱን ብዙ ጊዜ መሥዋዕት ለማድረግ ወደ ሰማይ አልገባም:: [26]እንዲህ ቢሆን ኖሮ፣ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ክርስቶስ ብዙ ጊዜ መከራን መቀበል ባስፈለገው ነበር:: አሁን ግን በዘመናት መጨረሻ ራሱን መሥዋዕት በማድረግ ኀጢአትን ለማስወገድ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ተገልጦአል:: [27]ሰው አንድ ጊዜ ሊሞት ከዚያም በኋላ በፍርድ ፊት ሊቆም ተወስኖበታል:: [28]ክርስቶስ የብዙ ሰዎችን ኀጢአት ለመሸከም፣ እንዲሁ አንድ ጊዜ መሥዋዕት ሆኖአል፤ ሁለተኛ ጊዜም ይገለጣል፤ ይህም ለሚጠባበቁት ድነትን ለማምጣት እንጂ ኀጢአትን ለመሸከም አይደለም::

**ክርስቶስ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ያቀረበው መሥዋዕት**

**10** ሕጉ ወደ ፊት ለሚመጡት መልካም ነገሮች ጥላ ነው እንጂ፣ እውነተኛው አካል አይደለም፤ ስለዚህም በየዓመቱ ዘወትር ያለማቋረጥ የሚቀርበው ተደጋጋሚ መሥዋዕት፣ ለአምልኮ የሚቀርቡትን ሰዎች ፍጹም ሊያደርጋቸው ከቶ አይችልም:: [2]ፍጹም ሊያደርጋቸው ቢችል ኖሮ፣ መሥዋዕት ማቅረቡን ይተዉት አልነበረምን? ደግሞም ለአምልኮ የሚቀርቡት ሰዎች ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ስለሚነጹ፣ በኅሊናቸው ኀጢአተኝነት ባልተሰማቸውም ነበር:: [3]ነገር ግን እነዚህ መሥዋዕቶች በየዓመቱ ኀጢአትን የሚያስታውሱ ናቸው፤ [4]ምክንያቱም የኮርማዎችና የፍየሎች ደም ኀጢአትን ማስወገድ አይችልም::

[5]ስለዚህ ክርስቶስ ወደ ዓለም በመጣ ጊዜ
 እንዲህ ብሎአል፤
"መሥዋዕትንና መባን አልፈልግህም፤
 ሥጋን ግን አዘጋጀህልኝ፤
[6]በሚቃጠል መሥዋዕትና ለኀጢአት በሚቀ

[ገ]16 ይህንን ትርጕም የሚሰጠው የግሪክ ቃል ኪዳን ተብሎም ሊተረጎም ይችላል፤ እንዲሁም ቍ 17

9፥18 ዘፀ24፥6-8
9፥19 ቍ12፤ዘፀ 24፥6-8፤ዕብ1፥1
9፥20 ዘፀ24፥8፤ ማቴ26፥28
9፥22 ዘፀ29፥21፤ ዘሌ8፥15፤17፥11
9፥23 ዕብ8፥5
9፥24 ቍ12፤ ሮሜ8፥34፤ ዕብ4፥14፤ዕብ8፥2
9፥25 ቍ7:8፤ ዕብ10፥19
9፥26 ቍ12:28፤ ዕብ4፥3፤7፥27፤ 1ዮሐ3፥5
9፥27 ዘፍ3፥19፤ 2ቆሮ5፥10
9፥28 ቍ12:26፤ ማቴ16፥27፤ 1ቆሮ1፥7፤ ዕብ5፥9፤7፥27፤ 1ጴጥ2፥24
10፥1 ቍ4:11፤ ቈላ2፥17፤ዕብ7፥19፤ 8፥5፤9፥11:23
10፥2 ዕብ9፥9
10፥3 ዘሌ16፥34፤ ዕብ9፥7
10፥4 ቍ1:11፤ ዕብ9፥12:13
10፥5 ዕብ1፥6፤2፥14፤ 1ጴጥ2፥24

የተብራራ ሐሳብ ነው:: ከክርስቶስ ቤዛዊ ሞት የተነሣ፣ ይህ ርስት በእግዚአብሔር ለተጠሩት ሁሉ ተዘጋጅቶላቸዋል (ከሮሜ 8፥28 ጋር ያነጻጽሩ):: *ቤዛ ሆኖ፤* ማር 10፥45 እና ማብ ይመ:: ደሙን በማፍሰስ በመጀመሪያው ኪዳን ሥር ሳሉ ከፈጸሙት ኀጢአት ነጻ ለማውጣት ተገቢውን ዋጋ ከፈለ::

9፥16 *ኑዛዜ፤* ይሄንኑ ቃል ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል ላይ "ኪዳን" (ቍ 15) ተብሎ ተተርጕሞአል፤ በዚህ ቍጥርና በቍ. 17 ላይ ግን ቃሉ የገባው የመጨረሻ ኑዛዜና ቃል ኪዳንን ለማመልከት ነው (ቍ18 ደግሞ "ኪዳን" ወደሚለው እሳቤ ይመለሳል):: ኑዛዜ የተገባላቸው ሰዎች ተናዛዡ እስኪሞት ድረስ ይገባኛል ማለት አይችሉም ቍ 17:: የክርስቶስ መሞት ፍጹም የተረጋገጠ በመሆኑ ኑዛዜ ያላቸው ሁሉ ተስፋ የተሰጠውን የዘላለም ርስት (ቍ 15) ለማግኘት ይችላሉ::

9፥18 *ያለ ደም፤* ያለ ሞት ማለት ሲሆን ሙሴ ብሉይ ኪዳንን ለማጽናት ደም ይወስድ የነበረው ከጥጃዎች ነበር::

*9፥19-20፤* እዚህ ላይ ስለ ተገለጸው ሥርዐት ዘጸ 24፥4-8 ይመ::

*9፥21፤* ዘሌ 8፥10:30 ይመ::

9፥23 *የሰማያዊው ነገሮች ምሳሌ፤* 8፥5 ይመ:: ምድራዊው ቤተ መቅደስ የሚነጻው በእንስሳት መሥዋዕት እንደ ሆነ ሁሉ፣ ሰማያዊው ቤተ መቅደስ የሚነጻውም የተሻለ መሥዋዕት በሆነው በክርስቶስ ነው::

9፥24 *አሁን ስለ እኛ በእግዚአብሔር ፊት ለመታየት፤* 7፥25፤ 1ዮሐ 2፥1 ይመ:: ታሪክ ሁሉ ፍጻሜውን ለማግኘት የሚገሠግሠው ወደዚሁ ነው::

9፥26 *በዘመናት መጨረሻ፤* መሲሑ ወደዚህ ምድር ሲመጣ የዘመኑ መጨረሻ ሆነ፤ ደግሞም ታሪክ ሁሉ ፍጻሜውን ለማግኘት የሚገሠግሠው ወደዚሁ ነው::

9፥27 *ሰው አንድ ጊዜ ሊሞት ከዚያም በኋላ በፍርድ ፊት ሊቆም ተወሥኖበታል፤* የተፈጥሮ ሕግ በመሆኑ ሰው አንድ ጊዜ ይሞታል (በኀጢአቱ ምክንያት፤ ሮሜ 5፥12)፤ ክርስቶስም የኀጢአት ፍጹም መሥዋዕት በመሆን አንድ ጊዜ ሞተ (ቍ 28):: ከሞት በኋላ ሰው በፍርድ ፊት እንደሚቆም ሁሉ ክርስቶስም ከሞተ በኋላ ከኀጢአትና ከፍርድ ሰዎችን ለማዳን እንደ ገና ይገለጣል:: (አማራጭ ትርጕሙን ይመ)::

9፥28 *ድነትን ለማምጣት፤* በመስቀል ላይ በመሞት የገዛውን (የተቤዠውን) ድነት ከሙሉ ክብሩ ጋር ያመጣዋል (ሮሜ 8፥29-30፤ ፊል 3፥20-21፤ 1ዮሐ 3፥2-3 ይመ):: *ለሚጠባበቁት፤* በስርየት ቀን እስራኤላውያን ሊቀ ካህኑ ከቅድስተ ቅዱሳን እስኪወጣ ድረስ እንደሚጠብቁት ሁሉ ነው:: (2ጢሞ 4፥8፤ቲቶ 2፥13 ይመ")

10፥1 *ሕጉ፤* ከሙሴ ሥርዐት ጋር ጥብቅ ቍርኝት ያለውን የሌዋውያኑን ክህነት ጨምሮ ነው (የ7፥11 ማብ ይመ):: *ጥላ ነው እንጂ፤* በሕጉ ላይ የተዘረዘሩት መሥዋዕቶች በሙሉ የሚያመለክቱት ክርስቶስ በመጣ ጊዜ የሚያቀርበውን መሥዋዕት ነው:: ስለዚህም በየዓመቱ መልሰው መላልሰው መሥዋዕት ማቅረብ ነበረባቸው፤ ይህም ፍጹም የሆነውና ኀጢአትን ማስወገድ የሚችለው መሥዋዕት ገና ያልቀረበ መሆኑን ይመሰክራል::

10፥4 *የኮርማዎችና የፍየሎች ደም ኀጢአትን ማስወገድ አይችልም::* የእንስሳት መሥዋዕት በእግዚአብሔር አምሳል ለተፈጠረው ሰው ብቁና ፍጹም መሆን አይችልም::

10፥5 *ክርስቶስ ወደ ዓለም በመጣ ጊዜ እንዲህ ብሎአል፤* ከዳዊት መዝሙር ላይ የተወሰዱት እነዚህ የዳዊት ቃላት (መዝ 40፥6-8)፣ ክርስቶስ ወደዚህ ምድር ሲመጣ ለአብ ያለውን ፍጹም ታዛዥነት ይገልጻሉ:: በሙሴ ሥርዐት የሚቀርቡት መሥዋዕቶች፣ ለእግዚአብሔር ፈቃድ ፍጹም ታዛዥ በሆነው ተተክተዋል (ቍ 17)::

10፥6 *ደስ አልተሰኘህም፤* እነዚህ መሥዋዕቶች ሥጋ የለበሰው የእግዚአብሔር ልጅ በመጣ ግዜ የሚያቀርበውን ፍጹምና የመጨረሻ መሥዋዕት የሚያመለክቱ ጊዜያዊና መንገድ

ርብ መሥዋዕት ደስ አልተሰኘህም::
[7]በዚያን ጊዜ እንዲህ አልሁ፤ ‘ስለ እኔ በመ
ጽሐፍ እንደ ተጻፈ፣
አምላክ ሆይ፤ እነሆኝ፤ ፈቃድህን ለማ
ድረግ መጥቻለሁ::’ ”ሉ

[8]ሕጉ ይህ እንዲደረግ ቢያዝም፣ እርሱ ግን በመጀመሪያ፣ “መሥዋዕትንና መባን፣ የሚቃጠል መሥዋዕትንና ስለ ኀጢአት የሚቀርበውን መሥዋዕት አልፈለግህም፤ ደስም አልተሰኘህበትም” ይላል:: [9]ቀጥሎም፣ “እነሆኝ፤ ፈቃድህን ለማድረግ መጥቻለሁ” አለ፤ ሁለተኛውን ለመመሥረት የመጀመሪያውን ሻረ:: [10]በዚህ ፈቃድ በኢየሱስ ክርስቶስ ሥጋ አማካይነት ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ በቀረበው መሥዋዕት ተቀድሰናል::

[11]ካህን ሁሉ በየዕለቱ ቆሞ አገልግሎቱን ያከናውናል፤ ኀጢአትን ማስወገድ ከቶ የማይችሉትን እነዚያኑ መሥዋዕቶች ዘወትር ያቀርባል:: [12]ይህኛው ካህን ግን አንዱን መሥዋዕት ለዘላለም አቅርቦ፣ በእግዚአብሔር ቀኝ ተቀምጦአል፤ [13]ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጠላቶቹ የእግሩ መረገጫ እስኪሆኑ ድረስ ይጠብቃል፤ [14]ምክንያቱም በአንዱ መሥዋዕት እነዚያን የሚቀደሱትን ለዘላለም ፍጹማን አድርጎአቸዋል::

[15]መንፈስ ቅዱስም ስለዚህ ነገር ይመሰክርልናል፤ በመጀመሪያ እንዲህ ይላል፤
[16]“ከዚያም በኋላ ከእነርሱ ጋር የምገባው
ኪዳን ይህ ነው፤
ይላል ጌታ፤
ሕጌን በልባቸው አኖራለሁ፤
በአእምሮአቸውም እጽፈዋለሁ::”
[17]ደግሞም፣
“ኀጢአታቸውንና ዐመፃቸውን፣
ከእንግዲህ አላስብም” ይላል::
[18]እነዚህ ይቅር ከተባሉ በኋላ ከእንግዲህ ስለ ኀጢአት የሚቀርብ መሥዋዕት አይኖርም::

## እስከ መጨረሻው ጸንቶ ስለ መገኘት የቀረበ ጥሪ

[19]እንግዲህ ወንድሞች ሆይ፤ በኢየሱስ ደም ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ለመግባት ድፍረት አግኝተናል፤ [20]ይኸውም በመጋረጃው ማለት በሥጋው በኩል በከፈተልን አዲስና ሕያው መንገድ ነው:: [21]በእግዚአብሔር ቤት ላይ የተሾመ ታላቅ ሊቀ ካህናት ስላለን [22]ከክፉ ኅሊና ለመንጻት ልባችንን ተረጭተን፣ ሰውነታችንንም በንጹሕ ውሃ ታጥበን፣ በእውነተኛ ልብና በሙሉ እምነት ወደ እግዚአብሔር እንቅረብ:: [23]የተስፋን ቃል የሰጠን ታማኝ ስለሆነ፣ እምነትን የምንናገርለትን ተስፋ አጥብቀን እንያዝ:: [24]እርስ በርሳችንም ለፍቅርና ለመልካም ሥራ እንዴት እንደምንነቃቃ እናስብ:: [25]አንዳንዶች ማድረጉን እንደተዉት መሰብሰባችንን አንተው፤ ይልቁንም ቀኑ እየተቃረበ መም

ሉ7 ሰብዓ ሊቃናት ይመ::

10፥7 ዕዝ6፥21 መዝ40፥6-8፤ ኤር36፥2፤ቴ26፥39
10፥8 ቁ5፥6፤ ማር12፥33
10፥9 ቁ7
10፥10 ቁ14፤ ኤፌ5፥26፤ዕብ2፥14፤ 7፥27፤ 1ጴጥ2፥24
10፥11 ቁ1፥4፤ ዕብ5፥1
10፥12 ማር16፥19፤ ዕብ5፥1
10፥13 ኢሱ10፥24፤ ዕብ1፥13
10፥14 ቁ1፥10፤ ኤፌ5፥26
10፥15 ዕብ3፥7
10፥16 ኤር31፥33፤ ዕብ8፥10
10፥17 ኤር31፥34፤ ዕብ8፥12
10፥19 ዘሌ16፥2፤ ኤፌ2፥18፤3፥12፤ ዕብ9፥8፤12፡25
10፥20 ዕብ6፥19፤ 9፥3፥8
10፥21 ዕብ2፥17፤ 3፥6
10፥22 ቁ1፤ ሕዝ36፥25፤ ሐሥ22፥16፤ኤፌ3፥12፤ ዕብ7፥19፤9፥14፤ 12፥24፤1ጴጥ1፥2
10፥23 1ቆሮ1፥9፤ ዕብ3፥1፡6
10፥24 ቲቶ2፥14
10፥25 ሐሥ2፥42፤ 1ቆሮ3፥13፤ዕብ3፥13

የሚያዘጋጁ ብቻ ናቸው::

10፥7 *ፈቃድህን ለማድረግ፤* የልጁ ምኞት የአብን ፈቃድ መፈጸም ነው (ሉቃ 22፥42፤ ዮሐ 4፥34 ይመ)::

10፥9 *ሁለተኛውን ለመመሥረት የመጀመሪያውን ሻረ፤* በፍጹም መታዘዝ ያቀረበው መሥዋዕት ከዚህ በፊት ይቀርቡ የነበሩ መሥዋዕቶችን በሙሉ ይተካል::

10፥10 *ተቀድሰናል፤* ጸድቀናል ደግሞም ለእግዚአብሔር ተለይተን ተሰጥተናል፤ አሁን የሚቀረው በየዕለቱ እየተቀደስን መሄድ ብቻ ነው (ቁ 14 ላይ “የሚቀደሱትን” የሚለውን ይመ፤ እንዲሁም የ1ቆሮ 1፥2 ማብ ይመ)::

*10፥11-14፤* “ቆመው” በሚያገለግሉትና ሥራውን ሁሉ ጨርሶ “በተቀመጠው” መካከል ያለውን ንጽጽር የሚያሳይ ክፍል ነው:: በሌዋውያኑ ሥርዐት የሚያገለግሉት ካህናት ሥራቸውን ገና ስላልጨረሱ ሁልጊዜ ቆመው ያገለግሉ ነበር::

10፥11 *እነዚያኑ መሥዋዕቶች ዘወትር ያቀርባል፤* ዘወትር እነዚያን መሥዋዕቶች የሚያቀርበው የተደነገገውን ነገር ሊፈጽሙ ስላልቻሉ ነው:: ኀጢአትንም ፈጽመው ማስወገድ ስለማይችሉ፣ በየጊዜው መቅረብ አለባቸው::

10፥12 *በእግዚአብሔር ቀኝ ተቀምጦአል፤* በሌዋውያኑ ሥርዐት መሠረት ከሚያገለግሉት ካህናት ጋር ሲነጻጸር ነው፤ እነርሱ ሥራቸውን አልጨረሱም (ቁ 11፤የ1፥3፤13 ማብ ይመ)፤ ክርስቶስ ግን ሥራውን ጨርሷል:: እርሱ አንድ ጊዜ ያቀረበው መሥዋዕት፣ ማንኛውም ሰውና በማንኛውም ዘመን የተፈጸመን ኀጢአት ማስተሰረይ ይችላል፤ ይህም ከእንዲህ በኋላ ምንም ዐይነት መሥዋዕት እንዳይኖር አድርጎአል (ቁ 14)::

*10፥15-18፤* በእነዚህ ቍጥሮች ላይ የተካተቱት ሁለቱ ጥቅሶች የተወሰዱት ከኤር 31፥31-34 (ቀደም ሲል በ8፥8-12 ላይ ተጠቅሰዋል) ላይ ነው:: አዲሱ ኪዳን ኀጢአት ሙሉ በሙሉ ይቅርታ እንደሚያገኝና (ቁ 17) ከዚህም የተነሣ ለኀጢአት የሚቀርብ መሥዋዕት ከዚህ በኋላ እንደማያስፈልግ ያረጋግጣል (ቁ 18)::

10፥19፤ ጸሐፊው የመልእክቱን ተደራሲዎች የሚያበረታታበት ሌላው ክፍል ነው (የ2፥1-4 ማብ ይመ):: *ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ለመግባት ድፍረት፤* የእንስሳቱ ደም ኀጢአታቸውን ፈጽሞ ሊያስተሰርይ ስለማይችል፣ በቀድሞው ኪዳን ሥር ለሚኖሩት ሕዝቦች ወደ እግዚአብሔር የሚወስደው መንገድ ተዘግቶ ነበር:: አሁን ግን ፍጹም የሆነው ካህን፣ ኀጢአትን ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ የሚያስተሰርይ ፍጹም መሥዋዕት ስላቀረበ፣ አማኞች ወደ ጸጋው ዙፋን መቅረብ ይችላሉ::

10፥20 *በመጋረጃው፣ ማለት በሥጋው፤* ኢየሱስ በሞተ ጊዜ፣ ቅድስተ ቅዱሳኑን ከቅድስት የሚለየው መጋረጃ፣ “ከላይ እስከ ታች ተቀዶ ሁለት ቦታ ተከፈለ” (ማር 15፥38):: መጋረጃው ሥቃዩን የሚገልጽ የክርስቶስ ሥጋ ምሳሌ ነው፤ ልክ እንደ መጋረጃው ሥጋውም በተቈረሰ ጊዜ ወደ እግዚአብሔር የሚወስደውን መንገድ ከፈተልን::

*10፥22-25፤* ኢየሱስ ካቀረበው መሥዋዕት የተነሣ ከአባቱ ጋር ለመታረቅ ቻልን፤ ጸሐፊው ይህን መሠረት በማድረግ ተደራሲዎቹን እንዲህ እያለ ያበረታታቸዋል፤ (1) ወደ እግዚአብሔር እንቅረብ፤ (2) “እምነትን የምንናገርለትን ተስፋ አጥብቀን እንያዝ” (3) “እርስ በርሳችንም ... እንዴት እንደምንነቃቃ እናስብ (4) “መሰብሰባችንን አንተው” (5) “እርስ በርሳችን እንበረታታ”::

*10፥22፤* ወደ እግዚአብሔር ለመቅረብ አራት ነገሮች መሟላት እንዳለባቸው ተገልጸአል:: (1) *በእውነተኛ ልብ፤* በውስጥ ሰውነት ፍጹም ታማኝ ሆኖ መገኘት፤ (2) *በሙሉ እምነት፤* ክርስቶስን አምኖ ለመከተል መወሰን፤ (3) *ከክፉ ኅሊና ለመንጻት ልባችንን ተረጭተን፤* ከበደለኛነት ስሜት ፍጹም ነጻ መሆን፤ ይህም ነጻነት ክርስቶስ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ባቀረበው መሥዋዕት ላይ የተመሠረተ መሆን አለበት፤ (4) *ሰውነታችንንም በንጹሕ ውሃ ታጥበን፤* እንደ ጥምቀት ያለውን ውጫዊ ሥርዐት ሳይሆን፣ ውስጣዊ መንጻትን የሚያመለክት ነው፤ ይህም በአሮጌው ኪዳን ሥር የነበሩ ካህናት ለመንጻት ያደርጉት የነበረውን ሥርዐት ያመለክታል:: (ዘፀ 30፥19-21፤ ዘሌ 8፥6 ይመ፤ እንዲሁም በሕዝ 36፥25 ላይ በአዲሱ ኪዳን የተገኘውን መንጻት ምሳሌያዊ በሆነ መንገድ ለመግለጽ የገባውን አባባል ይመ)::

10፥23 *የተስፋን ቃል የሰጠን ታማኝ ስለ ሆነ፤* ከ2ጢሞ 2፥13 ጋር ያነጻጽሩ:: *እምነትን የምንናገርለትን፤* 6፥18-20 ይመ:: *አጥብቀን፤* ያለ አንዳች ጥርጥር ወይም ማመንታት ማለት ነው:: ከመልእክቱ ተደራሲዎች ውስጥ አንዳንዶቹ ትግሉን ትተው ወደ ቀድሞው የይሁዲ እምነት ለመመለስ ከጅለው ነበር::

10፥25 *መሰብሰባችንን አንተው፤* “አንተው” የሚለውን ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል ጨርሶ ወይም እርግፍ አድርጎ መተውን ያመለክታል (ማቴ 27፥46፤ 2ቆሮ 4፥9፤ 2ጢሞ 4፥10፤ 16 ይመ):: *ቀኑ፤* ጌታ ዳግም ተመልሶ የሚመጣበትን ቀን ነው

ጣቱን ስታዩ እርስ በርሳችን እንበረታታ።
26የእውነትን ዕውቀት ከተቀበልን በኋላ
ሆን ብለን በኀጢአት ጸንተን ብንመላለስ፣
ከእንግዲህ ለኀጢአት የሚሆን ሌላ መሥ
ዋዕት አይኖርም፤ 27የሚቀረው ግን የሚያ
ስፈራ ፍርድና የእግዚአብሔርን ጠላቶች የሚ
በላ ብርቱ እሳት መጠበቅ ብቻ ነው።
28የሙሴን ሕግ የናቀ ማንኛውም ሰው ሁለት
ወይም ሦስት ሰዎች ከመሰከሩበት ያለ
ምሕረት ይገደል ነበር። 29ታዲያ የእግዚ
አብሔርን ልጅ የረገጠ፣ የተቀደሰበትን የኪ
ዳኑን ደም እንደ ተራ ነገር የቈጠረ፣ የጸ
ጋንም መንፈስ ያክፋፋ እንደምን ያለ የባሰ
ቅጣት ይገባው ይመስላችኋል? 30"በቀል የእኔ
ነው፤ እኔ ብድራትን እመልሳለሁ" ያለውን
እና ውቀዋለንና፤ ደግሞም፣ "ጌታ በሕዝቡ
ላይ ይፈርዳል" ይላል። 31በሕያው እግዚአብ
ሔር እጅ መውደቅ እጅግ የሚያስፈራ ነው።
32ብርሃን ከበራላችሁ በኋላ፣ በመከራ
ውስጥ በብርቱ ተጋድሎ ጸንታችሁ የቆ
ማችሁበትን የቀድሞውን ዘመን ዐስቡ።
33አንዳንድ ጊዜ በአደባባይ ለስድብና ለስ
ደት ተጋልጣችሁ ነበር፤ ሌላ ጊዜ ደግሞ
እንደዚህ ያለ መከራ ከደረሰባቸው ሰዎች
ጋር አብራችሁ መከራን ተቀብላችኋል።
34እናንተ ራሳችሁ የተሻለና ለዘወትር የሚ
ኖር ሀብት ያላችሁ መሆናችሁን ስለምታ
ውቁ ለታሰሩት ራራችሁ፤ ንብረታችሁም
ሲዘረፍ በደስታ ተቀበላችሁ።
35ስለዚህ ታላቅ ዋጋ ያለውን መታ መና
ችሁን አትጣሉ። 36የእግዚአብሔርን ፈቃድ ፈጽ
ማችሁ የተስፋ ቃሉን እንድትቀበሉ፣ ጸን
ታችሁ መቆም ያስፈልጋችኋል፤ 37ምክ
ንያቱም ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣
"የሚመጣው እርሱ ይመጣል፤ አይዘገይም።
38ጻድቅ ግን[h] በእምነት ይኖራል፤
ወደ ኋላ ቢያፈገፍግ፣
ነፍሴ በእርሱ ደስ አትሰኝም።"
39እኛ ግን አምነው ከሚድኑት ወገን እንጂ፣
ወደ ኋላ አፈግፍገው ከሚጠፉት አይደለንም።

## የእምነት ቋሚ ምስክሮች

11 እምነት ተስፋ ያደረግነው ነገር እንደ
ሚፈጸም እርግጠኛ የምንሆንበት፣ የማ
ናየውም ነገር እውን መሆኑን የምንረዳበት ነው።
2አባቶችም የተመሰከረላቸው በዚሁ ነው።
3ዓለማት በእግዚአብሔር ቃል እንደ ተፈጠሩ
በእምነት እንረዳለን፤ ስለዚህ የሚታየው
ነገር የተፈጠረው ከሚታየው እንዳልሆነ
እንገነዘባለን።
4አቤል ከቃየል ይልቅ የበለጠ መሥ
ዋዕት ለእግዚአብሔር በእምነት አቀረበ።
እግዚአብሔር ስለ ስጦታው በተናገረለት
ጊዜ፣ እርሱ በእምነት ጻድቅ እንደ ሆነ
ተመሰከረለት፤ ቢሞትም እንኳ እስከ አሁን
በእምነቱ ይናገራል።
5ሄኖክ ሞትን እንዳያይ ከዚህ ዓለም በእ
ምነት ተወሰደ፤ እግዚአብሔርም ስለ ወሰደው አልተ
ገኘም፤ ከመወሰዱም በፊት እግዚአብሔርን
ደስ እንዳሰኘ ተመስክሮለታልና። 6ደግሞም
ያለ እምነት እግዚአብሔርን ደስ ማሰኘት አይ
ቻልም፤ ምክንያቱም ወደ እግዚአብሔር የሚ
ቀርብ ሁሉ እግዚአብሔር መኖሩንና ከልብ
ለሚሹትም ዋጋ እንደሚሰጥ ማመን አለበት።
7ኖኅ ገና ስለማይታየው ነገር እግዚአብሔር
ባስጠነቀቀው ጊዜ፣ እግዚአብሔርን ፈርቶ
ቤተ ሰቦቹን ለማዳን መርከብን በእምነት ሠራ፤
በእምነቱ ዓለምን ኰነነ፤ በእምነትም የሚገ

10፥26 ዘፀ21፥14፤ ዘኍ15፥30፤ 1ጢሞ2፥4፤ዕብ5፥2፤ 6፥4-8፤2ጴጥ2፥20
10፥27 ኢሳ26፥11፤ 2ተሰ1፥7፤ ዕብ9፥27፤12፥29
10፥28 ዘዳ17፥6፡7፤ ማቴ18፥16፤ዕብ2፥2
10፥29 ማቴ4፥3፤ 26፥28፤1ቆሮ6፥11፤ ኤፌ4፥30፤ዕብ2፥3፤ 6፥4፡6፤12፥25፤ ራእ1፥5
10፥30 ዘዳ32፥35፡ 36፤መዝ135፥14፤ ሮሜ12፥19
10፥31 ኢሳ19፥16፤ ማቴ16፥16፤ 2ቆሮ5፥11
10፥32 ፊል1፥29፡ 30፤ዕብ6፥4
10፥33 1ቆሮ4፥9፤ ፊል4፥14፤1ተሰ2፥14
10፥34 ዕብ11፥16፤ 13፥3፤1ጴጥ1፥4፡5
10፥35 ኤፌ3፥12
10፥36 ሮሜ5፥3፤ ዕብ6፥15፤9፥15፤ 12፥1፤ያዕ1፥3፡4፡12፤ 5፥11፤2ጴጥ1፥6
10፥37 ማቴ11፥3፤ ራእ22፥20
10፥38 ሮሜ1፥17፤ ገላ3፥11፤ዕን2፥3፡ 4፤1፥1 2ቆሮ4፥18፤ዕብ3፥6
11፥2 ቍ4፡39
11፥3 ዘፍ1፤ዮሐ1፥3፤ ዕብ1፥2፤2ጴጥ3፥5
11፥4 ቍ2፡39፤ ዘፍ4፥4፤ዕብ12፥24፤ 1ዮሐ3፥12
11፥5 ዘፍ5፥21-24
11፥6 ዕብ7፥19

11፥7 ቍ1፤ ዘፍ6፥9፡ 13-22፤ሕዝ14፥14፡ 20፤ሮሜ9፥30፤ጴጥ3፥20

[h]38 ወይም *የእኔ ጻድቅ ግን*

(1ተሰ5፥2፤4፤2ተሰ1፥10፤2፥2፤2ጴጥ 3፥10 ይመ)።

*10፥26-31*፤ እነዚህ ቍጥሮች ከእግዚአብሔር ጉባኤ ተለ
ይተው የሚወጡ ሰዎችን (በቍ 25 ላይ "አንዳንዶች" የተባሉ
ትን) ለማስጠንቀቅ የተጻፉ ናቸው። በዚህ ክፍል ከተነገረው መንፈ
ሳዊ ውድቀት ጋር ተመሳሳይ ይዘት ያለውን የ6፥4-8 ማብ ይመ፤

10፥26 *ሆን ብለን በኀጢአት ጸንተን ብንመላለስ*፤
የክህደት ኀጢአትን ብንፈጽም ማለት ነው (ቍ 29 ይመ፤ የ5፥2
ማብ ይመ)። ይህ ጥቅስ የተመሠረተው በዘኍ 15፥27-31 ላይ
ነው። *ለኀጢአት የሚሆን ሌላ መሥዋዕት አይኖርም*፤ ክርስቶ
ስን ለኀጢአት ያቀረበውን መሥዋዕት አለመቀበል ማለት፣
ብቸኛ የሆነውን የኀጢአት መሥዋዕት አለመቀበል ማለት ነው፤
ከዚህ ሌላ መሥዋዕት የለምና።

10፥27 *የሚያስፈራ ፍርድና...የሚበላ ብርቱ እሳት*፤
2ተሰ 1፥6-9 ይመ።

*10፥28*፤ ዘዳ 17፥2-7 ይመ።

10፥29 *የኪዳኑን ደም*፤ 9፥20፤13፥20፤ ዘፀ 24፥8፤ ማቴ
26፥28፤ ማር 14፥24 ይመ።

*10፥31*፤ 12፥29 ይመ።

10፥32 *የቀድሞውን ዘመን*፤ ምናልባት መጀመሪያ
ወንጌልን በተቀበሉ ጊዜ የነበራቸውን ብርቱ አቋምና በዚያ ሁሉ
መከራ ውስጥ ሲያልፉ ያሳዩትን ጽናት እንዲሁም እርስ በርስ
የነበራቸውን ፍቅር ለመግለጽ ነው።

10፥34 *የተሻለና ለዘወትር የሚኖር ሀብት*፤ በክርስቶስ
ያገኙትን ድነትና ወደፊት የሚጠብቃቸውን ሽልማት ነው (11፥10፤
13-16፤26፤35፤13፥14፤ ማቴ 5፥11-12፤6፥19-21፤ ሮሜ 8፥18)።

10፥38 *ጻድቅ ግን በእምነት ይኖራል*፤ የዕንባቆም 2፥4
ማብ ይመ።

10፥39 *ወደ ኋላ አፈግፍገው ከሚጠፉት*፤ "አምነው
ከሚድኑት ወገን" ለሚለው ተቃራኒ ነው። የመልእክቱ ጸሓፊ
ከተደራሲዎቹ መካከል አብዛኞቹ አምነው ከሚድኑት ወገን እን
ደሆኑ እርግጠኛ ነው (የ6፥9 ማብ ይመ)።

*11፥1-12፥29*፤ ቀደም ሲል በተብራሩት የብሉይ ኪዳን
ክፍሎች ላይ የተመሠረተ ምክር ነው።

11፥2 *አባቶችም*፤ በቅድመ ክርስትና ዘመን የነበሩ የእም
ነት ዐርበኞች ናቸው፤ ከእነዚህም ውስጥ ጥቂቶቹ በዚህ ምዕራፍ
ተጠቅሰዋል።

*11፥4*፤ ዘፍ 4፥2-5 ይመ። *ጻድቅ እንደ ሆነ ተመሰ
ከረለት*፤ ሁለቱ ወንድማማቾች፣ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት
አቀረቡ፤ ቃየን ከዕርሻው ፍሬ ሲያቀርብ፣ አቤል ደግሞ ከበጎቹ
መካከል በኵር የሆነውን አቀረበ። የአቤል መሥዋዕት ተቀባይ
ነት ሊያገኝ የቻለበት ዋናው ምክንያት፣ መሥዋዕቱን "በእም
ነት" ስላቀረበ ነው። ይህም የቃየል መሥዋዕት ተቀባይነት
ያጣው በእምነት ሳይሆን ለታይታ ብቻ የቀረበ መሆኑን ያስገነዝ
ባል (የዘፍ 4፥3-4 ማብ ይመ)።

11፥5 *ሄኖክ* ዘፍ 5፥18-24 ይመ። *ተወሰደ*፤ እግዚአብሔር
ወደ ሚኖርበት ነው (የዘፍ 5፥24 ማብ ይመ፤ ከመዝ 49፥15፤
73፥24 ጋር ያነጻጽሩ)።

11፥6 *ያለ እምነት እግዚአብሔርን ደስ ማሰኘት አይቻ
ልም*፤ ሄኖክ እግዚአብሔርን ደስ ማሰኘቱ እምነት ያለው ሰው
መሆኑን ያረጋግጣል። *ማመን አለበት*፤ እምነት የሚያርፍበት
ወይም የሚቆምበት ነገር ያስፈልገዋል፤ የእውነተኛ እምነት ማረ
ፊያ እግዚአብሔር ነው። *ከልብ ለሚሹትም*፤ ኤር 29፥13 ይመ።

11፥7 *ኖኅ*፤ ዘፍ 5፥28-9፥29 ይመ። *በእምነቱ*፤ የጥፋት
ውሃ በመጣ ጊዜ፣ የእግዚአብሔር ቃል እውነተኛ መሆኑ

ኘውን ጽድቅ ወራሽ ሆነ።

[8]አብርሃም ርስት አድርጎ ወደሚቀበለው ስፍራ እንዲሄድ በተጠራ ጊዜ በእምነት ታዘዘ፤ ወዴት እንደሚሄድ ባያውቅም፣ እሺ ብሎ ሄደ። [9]በባዕድ አገር እንዳለ መጻተኛ በተስፋዪቱ ምድር በእምነት ተቀመጠ፤ የተስፋውን ቃል አብረውት እንደሚወርሱት እንደ ይስሐቅና እንደ ያዕቆብ በድንኳን ኖረ፤

[10]ምክንያቱም መሠረት ያላትን፣ እግዚአብሔር የሠራትንና የፈጠራትን ከተማ ይጠባበቅ ነበር። [11]አብርሃም[ኸ] ምንም እንኳ ዕድሜው ቢገፋም፣ ሣራም[ኸ] ራሷ መካን ብትሆንም፣ ተስፋን የሰጠውን ታማኝ አድርጎ ስለ ቈጠረ[ኸ] በእምነት የልጅ አባት ለመሆን በቃ። [12]ስለዚህ እንደ ሞተ ሰው ከሚቈጠር ከዚህ ከአንድ ሰው፣ እንደ ሰማይ ከዋክብት የበዛና እንደ ባሕር ዳር አሸዋ ተቈጥሮ የማያልቅ ዘር ተገኘ።

[13]እነዚህ ሁሉ የተሰጣቸውን የተስፋ ቃል ሳያገኙ እምነታቸውን እንደ ጠበቁ ሞቱ፤ ሆኖም ከሩቅ አይተው ሰላም አሉት፤ በዚህ ምድር ሲኖሩ መጻተኞችና እንግዶች መሆናቸውን ተገንዝበው ነበርና። [14]እንደዚህ የሚሉት ሰዎች የራሳቸው የሆነውን አገር እንደሚጠባበቁ ያሳያሉ። [15]ትተውት የወጡትን አገር ቢያስቡ ኖሮ፣ ወደዚያ የመመለስ ዕድል ነበራቸው። [16]አሁን ግን ከዚህ የሚበልጠውን ሰማያዊ አገር ይናፍቃሉ፤ ስለዚህ እግዚአብሔር አምላካቸው ተብሎ ሊጠራ አላፈረም፤ ከተማን አዘጋጅቶላቸዋልና።

[17]አብርሃም እግዚአብሔር በፈተነው ጊዜ፣ ይስሐቅን መሥዋዕት አድርጎ በእምነት አቀረበ፤ የተስፋን ቃል የተቀበለው እርሱ፣ አንድ ልጁን ሊሠዋ ዝግጁ ነበር፤ [18]ይህም እግዚአብሔር፣ "ዘርህ በይስሐቅ ይጠራል" ያለለት ነበር። [19]አብርሃም እግዚአብሔር ሙታንን ሊያስነሣ እንደሚችል ተገንዝቦ ነበር፤ ይስሐቅንም ከሞት የመነሣት አምሳያ ሆኖ አገኘው።

[20]ይስሐቅ ወደፊት የሚሆነውን ዐስቦ ያዕቆብንና ዔሳውን በእምነት ባረካቸው።

[21]ያዕቆብ በሚሞትበት ጊዜ እያንዳንዳቸውን የዮሴፍን ልጆች በእምነት ባረካቸው፤ በበትሩም ጫፍ ዘንበል ብሎ ሰገደ።

[22]ዮሴፍ ሊሞት በተቃረበ ጊዜ፣ ስለ እስራኤል ሕዝብ ከግብፅ መውጣት በእምነት ተናገረ፤ ስለ ዐጽሙም ትእዛዝ ሰጠ።

[23]ሙሴ ከተወለደ በኋላ፣ ወላጆቹ መልከ መልካም ሕፃን መሆኑን ስላዩ በእምነት ሦስት ወር ሸሸጉት፤ የንጉሡንም ዐዋጅ አልፈሩም።

[24]ሙሴ ካደገ በኋላ፣ የፈርዖን የልጅ ልጅ መባልን በእምነት እምቢ አለ። [25]ለጥቂት ጊዜ በኀጢአት ከሚገኝ ደስታ ይልቅ፣ ከእግዚአብሔር ሕዝብ ጋር መከራን መቀበል መረጠ። [26]ከግብፅ ሀብት ይልቅ ስለ ክርስቶስ መከራን መቀበል እጅግ የሚበልጥ ሀብት መሆኑን ተገነዘበ፤ ወደ ፊት የሚቀበለውን ብድራት ከሩቅ ተመልክቶ

11፥8 ዘፍ12፥1-4፡7፤ሐሥ7፥2-4
11፥9 ዘፍ12፥8፤18፥1፡9፤ሐሥ7፥5፤ዕብ6፥17
11፥10 ቍ.16፤ ዕብ12፥22፤13፥14፤ ራእ21፥2፡14
11፥11 ዘፍ17፥17-19፤ 18፥11-14፤ 21፥2፤1ቆሮ1፥9
11፥12 ዘፍ22፥17፤ ሮሜ4፥19
11፥13 ቍ.39፤ ዘፍ23፥4፤ዘሌ25፥23፤ ማቴ13፥17፤ሉቃ3፥20፤ 1ጴጥ1፥17፤2፥11
11፥15 ዘፍ24፥6-8
11፥16 ቍ.10፤ ዘፍ26፥24፤28፥13፤ ዘፀ3፥6፡15፤ማር8፥38፤ 2ጢሞ4፥18፤ዕብ13፥14
11፥17 ዘፍ22፥1-10፤ ያዕ2፥21
11፥18 ዘፍ21፥12፤ ሮሜ9፥7
11፥19 ሮሜ4፥21፤ ዮሐ5፥21
11፥20 ዘፍ27፥27-29፡ 39፡40
11፥21 ዘፍ48፥1፡ 8-22
11፥22 ዘፍ50፥24፡ 25፤ዘፀ13፥19፤ ኢያ24፥32
11፥23 ዘፀ1፥16፡ 22፤2፥2
11፥24 ዘፀ2፥10፡11
11፥25 ቍ.37
11፥26 ሉቃ14፥33፤ዕብ10፥35፤13፥13

ኸ11 *ወይም ሣራ ... አብርሃምም ... ስለቈጠረች*

ተረጋገጠ፤ የኖኅ እምነት ትክክለኛ እንደ ሆነ ተመሰከረ፤ የዓለምም ክህደት ተኰነነ። *በእምነትም የሚገኘውን ጽድቅ፤* ኖኅ ምንም እንኳ የተነገረው ነገር ይኸውም የጥፋት ውሃ ባይታየው (ቍ. 7) በእግዚአብሔርና በቃሉ ላይ ያለውን ሙሉ እምነት ገለጸ። ስለዚህ ኖኅ በእምነት ከሚኖሩ የእግዚአብሔር ጻድቃን መካከል ለመቈጠር በቃ (10፥38)። በእግዚአብሔር ቃል ላይ ያለው እምነት በደረቅና የሠራውን መርከብ ማንሳፈፍ የሚችል በቂ ውሃ ይኖራል ተብሎ በማይታሰብበት ስፍራ መርከብን እንዲሠራ አነሣሣው።

11፥8 *አብርሃም፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ በ"እምነት" ለሚኖሩና "ለሚያምኑ ሁሉ አባት" ተብሎ ተጠቅሶአል (ሮሜ 4፥11-12፤16፤ገላ3፥7፤9፤29)። *በተጠራ ጊዜ፤* ዘፍ 12፥1-3 ይመ። እምነቱ የታየው በመታዘዙ ነው (የዘፍ 12፥4 ማብ ይመ)። *ርስት አድርጎ ወደሚቀበለው ስፍራ፤* ወደ ከነዓን ነው። *ወዴት እንደሚሄድ ባያውቅም፤* አካሄዱ ባወጣ ያውጣው በሚል ጭፍንነት ሳይሆን የእግዚአብሔርን ታማኝነት በመታመን ነበር።

11፥10 *መሠረት ያላትን ... ከተማ፤* የቀድሞ አባቶች ይኖሩባት ከነበረው ጊዜያዊ ድንኳን ጋር በማነጻጸር ነው (ቍ. 9)። ይህች ከተማ "ሰማያዊት ኢየሩሳሌም" (12፥22)፣ "ወደፊት የምትመጣዋ ከተማ" (13፥14) እንዲሁም "አዲሲቱ ኢየሩሳሌም" (ራእ 21፥2-4፤9-27) ናት። *የፈጠራትን፤* ከመዝ 147፥2 ያነጻጽሩ። የኢሳ 62፥5 አማራጭ ትርጕሙን ይመ።

11፥11 *ሣራም ... መካን ብትሆንም፤* ምናልባት ልጅ መውለድ የማትችልበት ዕድሜ ላይ መድረሷን ያመለክታል (ዘፍ 18፥11-12፤ የዘፍ 11፥30 ማብ ይመ)።

11፥12 *እንደ ሞተ ሰው፤* ምክንያቱም ዕድሜው መቶ ዓመት ሆኖት ነበር (ዘፍ 21፥5፤ ሮሜ 4፥19 ይመ)። *እንደ ሰማይ ከዋክብት... እንደ ባሕር ዳር አሸዋ፤* ዘፍ 13፥16 እና ማብራሪያውን ይመ፤ እንዲሁም 15፥5፤22፥17፤26፥4፤1ነገ 4፥20 ይመ።

11፥13 *ከሩቅ አይተው ሰላም አሉት፤* በድንግዝግዝ ቢሆንም፣ ይህን ሰማያዊ እውነት በእምነት ተመለከቱ፤ ደግሞም ተስፋ ያደረጉትን ነገር በመጨረሻ እንደሚያገኙ እርግጠኛ ነበሩ (ቍ. 1 ይመ)። *በዚህ ምድር ሲኖሩ መጻተኞችና እንግዶች፤* እውነተኛ ቤታቸው በሰማይ ነው።

11፥14 *የራሳቸው የሆነውን፤* የተሻለና ሰማያዊ አገርን ያመለክታል (ቍ. 16)።

11፥16 *ከተማ አዘጋጅቶላቸዋልና፤* ከተማና (ቍ. 10) አገር የሚሉት ቃላት በዚህ መልእክት መደምደሚያ ምዕራፎች ውስጥ በተለዋዋጭነት ገብተዋል (ቍ. 9-10፡14-16፤ 13፥14)። በዮሐንስ ራእይ ውስጥ ይህች ከተማ፣ አማኞች የሚኖሩባት አዲሲቱ ኢየሩሳሌም ተብላለች (ራእ 21፥2 ይመ)።

*11፥17፤* ዘፍ 22 ይመ። *አንድ ልጁን፤* ዘፍ 22፥2፤12፤16፤ ዮሐ 3፥16፤ ሮሜ 8፥32 ይመ።

11፥19 *እግዚአብሔር ሙታንን ሊያስነሣ እንደሚችል፤* የአብርሃም እምነት ጠንካራ ከመሆኑ የተነሣ፣ እግዚአብሔር ከወደደ ይስሐቅን ከሞት እንኳ ሊያስነሣው እንደሚችል አምኖአል፤ ይህም ምትክ የሚሆነው በግ በቀረበ ጊዜ ምሳሌያዊ በሆነ መንገድ ተፈጽሞአል። (ዘፍ 22፥13)።

*11፥20፤* ዘፍ 27፥27-40 ይመ።

*11፥21፤* ዘፍ 47፥29-31፤ 48፥8-20 ይመ።

*11፥22፤* ዘፍ 50፥24-25 ይመ። ያዕቆብና (ቍ. 21) ዮሴፍ በሕይወት ዘመናቸውም ሆነ በሞታቸው፣ በእምነት ጠንካራ ለነበሩ ሰዎች ተጨማሪ ምሳሌ ሆነው ቀርበዋል (ቍ. 13)።

*11፥23-29፤* ሐሥ 7፥20-44 ይመ።

11፥23 *ወላጆቹ፤* ዘፀ 6፥20፤ ዘኍ 26፥58-59 ይመ። *መልከ መልካም ሕፃን መሆኑን፤* የዘፀ 2፥2 ማብ ይመ። *የንጉሡንም ዐዋጅ፤* ወንድ ሆነው የሚወለዱ እስራኤላውያንን በሙሉ ለመግደል የወጣ ዐዋጅ ነው (ዘፀ 1፥16፤22)።

11፥25 *በኀጢአት ከሚገኝ ደስታ፤* በግብፅ ቤተ መንግሥት ውስጥ ከሚገኝ ድሎትና ክብር ነው።

11፥26 *ስለ ክርስቶስ፤* ሙሴ ስለ መሲሑ ተስፋ የነበረው ዕውቀት ውሱን ቢሆንም፣ ይህ ተስፋ እውን ከሚሆንበት ሕዝብ ጋር መሆንን መረጠ። *ከግብፅ ሀብት፤* እጅግ ብዙ ሀብት ፈሶበት የተሠራው የንጉሥ ቱታካሙን መቃብር፣ በብዙ ሺህ ኪሎ ግራም የሚቈጠር ንጹሕ ወርቅ ፈጅቷል።

11፥27 *ግብፅን ለቆ በእምነት ወጣ፤* ምናልባት የአርባ ዓመት

አልና:: [27]የንጉሡን ቍጣ ሳይፈራ ግብፅን ለቆ በእምነት ወጣ፤ የማይታየውንም እንዳየው አድርጎ በመቍጠር በሐሳቡ ጸና:: [28]በኩሮች የሆኑትን የሚገድለው ቀሣፊ የእስራኤልን በኵር ልጆች እንዳይገድል ፋሲካን በእምነት አደረገ፤ ደምንም ረጨ::

[29]ሕዝቡ በደረቅ መሬት እንደሚኬድ ቀይ ባሕርን በእምነት ተሻገሩ፤ ግብፃውያን ግን እንደዚሁ ለማድረግ ሲሞክሩ ሰጠሙ::

[30]ሕዝቡ የኢያሪኮን ግንብ ሰባት ቀን ከዞሩት በኋላ፣ በእምነት ወደቀ::

[31]ዝሙት አዳሪዋ ረዓብ፣ ሰላዮቹን በሰላም ስለ ተቀበለቻቸው ከማይታዘዙት° ጋር ያልጠፋችው በእምነት ነው::

[32]እንግዲህ ከዚህ በላይ ምን ልበል? ስለ ጌዴዎን፣ ስለ ባርቅ፣ ስለ ሳምሶን፣ ስለ ዮፍታሔ፣ ስለ ዳዊት፣ ስለ ሳሙኤል፣ እንዲሁም ስለ ነቢያት እንዳልተርክ ጊዜ የለኝም:: [33]እነዚህ በእምነት መንግሥታትን ድል ነሡ፤ በቅን ፈረዱ፤ የተሰጠውን የተስፋ ቃል ተቀበሉ፤ የአንበሶችን አፍ ዘጉ፤ [34]የእሳትን ኀይል አጠፉ፤ ከሰይፍ ስለት አመለጡ፤ ከድካማቸው በረቱ፤ በጦርነት ኀያል ሆኑ፤ ባዕዳን ወታደሮችን አባረሩ:: [35]ሴቶች ሙታናቸው ተነሡላቸው:: ሌሎቹ ደግሞ የተሻለውን ትንሣኤ ለማግኘት ሲሉ፣ መትረፍን ንቀው ለሞት ለሚዳርግ ሥቃይ ራሳቸውን ሰጡ፤ ከዚህም ነጻ ለመውጣት አልፈለጉም:: [36]አንዳንዶቹ መዘባበቻ ሆኑ፤ ተገረፉ:: ሌሎቹ ደግሞ ታስረው ወደ ወህኒ ተጣሉ፤ [37]በድንጋይ ተወገሩ፤ በመጋዝ ለሁለት ተሰነጠቁ፤° በሰይፍ ተወግተው ሞቱ፤ እየተንከራተቱ፣ እየተሰደዱና እየተንገላቱ የበግና የፍየል ቈዳ ለብሰው ዞሩ፤ [38]ዓለም ለእነርሱ አልተገባቻቸውምና:: በየበረሓውና በየተራራው፣ በየዋሻውና በየጕድጓዱ ተንከራተቱ ::

[39]እነዚህ ሁሉ ስለ እምነታቸው የተመሰከረላቸው ቢሆኑም ከእነርሱ ማንም የተስፋውን ቃል የተቀበለ የለም:: [40]እግዚአብሔር ለኛ የሚበልጥ ነገር ስላዘጋጀ፣ ያለ እኛ ፍጹማን ሊሆኑ አልቻሉም::

## እግዚአብሔር ልጆቹን ይቀጣል

**12** እንግዲህ እነዚህን የመሳሰሉ ብዙ ምስክሮች እንደ ደመና በዙሪያችን ካሉልን፣ ሸክም የሚሆንብንን ሁሉ፣ በቀላሉም ተብትቦ የሚይዘንን ኀጢአት አስወግ

11፥27 ዘፀ12፥50፡51
11፥28 ዘፀ12፥21-23፤ 1ቆሮ10፥10
11፥29 ዘፀ14፥21-31
11፥30 ኢያ6፥12-20
11፥31 ኢያ2፥1፡9-14፤ 6፥22-25፤ያዕ2፥25
11፥32 መሳ4-5፤ 6-8፤11-12፤13-16፤ 1ሳሙ1፥20፤16፥1፡13
11፥33 ዳን6፥22፤ 2ሳሙ8፥1-3
11፥34 ዘፀ18፥4፤ መሳ15፥8፤2ዜና20፥7፤ ዳን3፥19-27
11፥35 1ነገ17፥22፡ 23፤2ነገ4፥36፡37
11፥36 ዘፍ39፥20፤ ኤር20፥2፤37፥15
11፥37 1ነገ19፥10፤ 2ነገ1፥8፤2ዜና24፥21፤ ኤር26፥23
11፥38 1ነገ18፥4፤ 19፥9
11፥39 ቍ2፡4፡ 13፤ዕብ10፥36
11፥40 ዕብ2፥10፤ ራእ ፥11
12፥1 1ቆሮ9፥24፤ ዕብ10፥36

°31 ወይም *ከማያምኑት*
°37 አንዳንድ የጥንት ቅጆች *በድንጋይ ተወገሩ፤ ለፈተና አልፈው ተሰጡ፤*

ሰው በሆነው ጊዜ በሲና ባሕር ስርጥ ወደምትገኘው የምድያም ምድር የኮበለለበትን ሁኔታ ያመለክታል (ዘፀ 2፥11-15፤ ሐሥ 7፥23-29):: *የንጉሡን ቍጣ ሳይፈራ፤* በዘፀአት መጽሐፍ ውስጥ ሙሴ ፈርቶ እንደ ነበር ተገልጸአል (ዘፀ 2፥14)፤ ነገር ግን ማንን እንደ ፈራ በግልጽ አልተነገረም:: ደግሞም ፈርዖን ሊገድለው ባሰበ ጊዜ ከፈርዖን እንደ ሸሸ ተገልጸአል (ዘጸ2፥15)፤ ነገር ግን የሸሸው ከፍርሀት የተነሣ እንደ ሆነ ግልጽ አይደለም:: የዕብራውያን መልእክት ጸሓፊ ይህን ሁኔታ መሠረት በማድረግ፣ ሙሴ ከፈርዖን ሲሸሽ በእግዚአብሔር ታምኖ እንደ ነበር፣ እስራኤልም ነጻ የምትወጣበት ቀን እንደ መጣና እርሱም የበኩሉን ድርሻ ለመፈጸም እንደ ተጠራ ይነግረናል:: *በሐሳቡ ጸና፤* ለአርባ ዓመት በምድያም ቈየ (ሐሥ 7፥30)::

*11፥28፤* ዘፀ 12 ይመ::

*11፥29፤* ዘፀ 14-15 ይመ:: ሙሴ ሦስተኛውንና የመጨረሻውን አርባ ዓመት ያሳለፈው እስራኤላውያንን በምድረ በዳ ሲመራ ነው:: ዕድሜው መቶ ሃያ ዓመት ሲሆነው በሞዓብ ሞተ (ዘዳ 34፥1-7)::

*11፥30፤* ሙሴ ሲመራው የነበረውን ሕዝብ ኢያሱ ተረከበ፤ እርሱም ሕዝቡን ወደ ተስፋዪቱ ምድር አደረሰ:: *ኢያሪኮ፤* የተስፋዪቱን ምድር ለመውረስ በወጡበት ጊዜ የገጠማቸውን ትልቁን ጠላት ያለ አንዳች ጦርነት በእምነት ብቻ ድል ነሡ (ኢያ 6)::

11፥31 *ዝሙት አዳሪዋ ረዓብ፤* አዲስ ወዳገኘችው እምነት ከመምጣቷ በፊት የነበራትን የቀድሞ ሕይወቷን የሚያመለክት አገላለጽ ነው (ኢሱ 2፥8-11፤ 6፥22-25)፤ ከዚህም በላይ ወሰን የሌለው የእግዚአብሔር ጸጋ፣ ማንኛውንም ኀጢአተኛ ተቤዥቶ ለዘላለም ክብር ማብቃት እንደሚችል የሚያሳይም ነው:: *ሰላዮቹን በሰላም ስለ ተቀበለቻቸው፤* ያዕ 2፥25 ይመ::

*11፥32-38፤* ክርስቶስ ከመምጣቱ በፊት አያሌ የእምነት ዐርበኞች ነበሩ፤ ስለ እነርሱም ብዙ መጻፍ ይቻል ነበር:: ለአብነት ያህል ግን በእምነታቸው የታወቁ ጥቂት ወንዶችና ሴቶች ተወስተዋል:: ሁሉንም አንድ የሚያደርጋቸው ነገር ቢኖር፣ በእምነት ድል መንሣታቸው ነው (ቍ 33)::

11፥32 *እንዳልተርክ* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል ተባዕት ጾታ ሲሆን፣ ይህም የዕብራውያን መልእክት ጸሓፊ በጾታው ወንድ እንደ ሆነ ያሳያል (በመልእክቱ መግቢያ ላይ "ጸሓፊው" የሚለውን ይመ):: *ስለጌዴዎን፤ ስለባርቅ፤ ስለ ሳምሶን፤ ስለ ዮፍታሔ፤* መሳ 4፥6-5፥15፤6፥11-8፥35፤11፥-12፥7፤ 13፥24-16፥31 ይመ:: *ስለ ሳሙኤል፣ እንዲሁም ስለ ነቢያት፤* መዝ 99፥6፤ ኤር 15፥1፤ ሐሥ 3፥24፤ 13፥20 ይመ::

11፥33 *የአንበሶችን አፍ፤* በአንበሶች ጒድጓድ ውስጥ ከተጣለው ዳንኤል ጋር ያነጻጽሩ (ዳን 6)::

11፥34 *የእሳትን ኀይል አጠፉ፤* በእሳት እቶን ውስጥ ተጥለው ከነበሩት ከዳንኤል ባልንጀሮች ከሲድራቅ፣ ከሚሳቅና ከአብድናጎም ጋር ያነጻጽሩ (ዳን 3):: *ከድካማቸው በረቱ፤* በእግዚአብሔር ርዳታ ነው (ሮሜ 8፥26፤ 2ቆሮ 12፥9 ይመ)::

11፥35 *ሴቶች ሙታናቸው ተነሡላቸው፤* ከሰራፕታዋ መበለት (1ነገ 17፥17-24) እንዲሁም ከሱናማዊቷ ሴት (2ነገ 4፥8-36) ጋር ያነጻጽሩ:: *የተሻለውን ትንሣኤ ለማግኘት ሲሉ መትረፍን ንቀው ለሞት ለሚዳርግ ሥቃይ ራሳቸውን ሰጡ፤ ከዚህም ነጻ ለመውጣት አልፈለጉም፤* ከክርስቶስ ልደት በፊት በሁለተኛው ምእተ ዓመት ላይ በግፍ የተገደሉትን የመቃብያንን አይሁድ ዐርበኞች የሚያስታውስ ነው (2መቃብያን 7 ይመ):: ይሁንና እዚህ ላይ የተባለው ነገር በብርቱ ሥቃይ ውስጥ ሲያልፉ፣ በእግዚአብሔር ላይ ባላቸው እምነት ጸንተው የቆሙትን ስፍር ቍጥር የሌላቸውንና በስም የሚታወቁትንም ሆነ የማይታወቁትን አማኞች ሊያመለክት ይችላል::

11፥37 *በድንጋይ ተወገሩ፤* እውነት በመናገራቸው የተገደሉትን እንደ ካህኑ ዮዳሄ ልጅ እንደ ዘካርያስ ያሉትን ነው (2ዜና 24፥20-22፤ ሉቃ 11፥51):: እንዲሁም የኤርምያስ መጽሐፍን መግቢያ ይመ:: *በመጋዝ ለሁለት ተሰነጠቁ፤* በጨካኙ ንጉሥ በምናሴ እጅ እንደ ሞተ በአፈ ታሪክ የሚነገርለትን ኢሳይያስን ሊሆን ይችላል (የትንቢተ ኢሳይያስን መግቢያ ይመ)::

11፥39 *እነዚህ ሁሉ ስለ እምነታቸው የተመሰከረላቸው ቢሆኑም፤* ሁሉም የእምነት ዐርበኞች የገጠማቸውን ፈተና ወዲያውኑ በድል ባይወጡም፣ ሁሉም ግን በእግዚአብሔር ተባርከዋል::

11፥40 *እግዚአብሔር ... የሚበልጥ ነገር ስላዘጋጀ፤* ለእኛም እንደ ሆነው ሁሉ ለእነርሱም የሰጠው ተስፋ የሚፈጸመው "ትንሣኤና ሕይወት" በሆነው በክርስቶስ ነው (ዮሐ 11፥25-26):: እነርሱ ያለ እኛ ፍጹማን ሊሆኑ አይችሉም፤ ከዚህ በፊት የነበሩ ሰዎች ሁሉ ትኩር ብለው ይመለከቱ የነበረው እግዚአብሔርንና የተስፋ ቃሉን ነበር:: እግዚአብሔር የሰጣቸው ተስፋ አሁን በኢየሱስ ክርስቶስ እውን ሆነ፤ መዳናቸውም እውን የሆነው በእርሱ በኩል ነው::

12፥1 *እነዚህን የመሳሰሉ ብዙ ምስክሮች እንደ ደመና በዙሪያችን ካሉልን፤* እዚህ ላይ የሚታየው ምስል በአንድ ትልቅ ቤተ ተውኔት ውስጥ የሚደረገውን ውድድር ይመስላል:: ምስክሮች የተባሉት በምዕራፍ 11 ላይ የተጠቀሱት የእምነት ዐርበኞች ናቸው:: እነርሱም ትርኢት ተመልካች ሳይሆኑ እውነተኛ ምሳሌዎች ናቸው:: ምስክሮች የሚለውን ቃል ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል "ሰማዕታት" የሚል ትርጒም አለው:: ሲመሰክሩ የነበረውም ስለ እምነት ኀይልና ስለ የእግዚአብሔር ታማኝነት

ደን በፊታችን ያለውን ሩጫ በጽናት እንሩጥ። 2የእምነታችን ጀማሪና ፍጹም አድራጊ የሆነውን ኢየሱስን እንመልከት፤ እርሱ በፊቱ ስላለው ደስታ መስቀሉን ታግሦ፣ የመስቀሉንም ውርደት ንቆ በእግዚአብሔር ዙፋን ቀኝ ተቀምጦአል። 3እንግዲህ ዝላችሁ ተስፋ እንዳትቈርጡ፣ ከኀጢአተኞች የደረሰበትን እንዲህ ያለውን ተቃውሞ የታገሠውን እርሱን ዐስቡ።

4ከኀጢአት ጋር ስትታገሉ ገና ደማችሁን እስከ ማፍሰስ ድረስ አልተቃወማችሁም። 5ልጆች እንደመሆናችሁ እንዲህ በማለት የተናገራችሁን ማበረታቻ ቃልም ረስታችኋል፦

“ልጄ ሆይ፤ የጌታን ቅጣት አታቃል፤
 በሚገሥጽህም ጊዜ ተስፋ አትቍረጥ፤
6ምክንያቱም ጌታ የሚወደውን ይገሥጻል፤
 እንደ ልጅ የሚቀበለውንም ይቀጣል።”

7እግዚአብሔር እንደ ልጆቹ ይዞአችኋልና የተግሣጽን ምክር ታገሡ፤ ለመሆኑ አባቱ የማይቀጣው ልጅ ማን ነው? 8ልጆች ሁሉ በሚቀጡበት ቅጣት ተካፋይ ካልሆናችሁ፣ ዲቃሎች እንጂ ልጆች አይደላችሁም። 9ከዚህም በላይ፣ እኛ ሁላችን የሚቀጡን ምድራዊ አባቶች ነበሩን፤ እናከብራቸውም ነበር። ታዲያ ለመናፍስት አባት እንዴት አብልጠን በመገዛት በሕይወት አንኖርም? 10አባቶቻችን መልካም መስሎ እንደታያቸው ለጥቂት ጊዜ ይቀጡን ነበር፤ እግዚአብሔር ግን የቅድስናው ተካፋዮች እንድንሆን ለእኛ ጥቅም ሲል ይቀጣናል።

11ቅጣት ሁሉ በወቅቱ የሚያሳዝን እንጂ ደስ የሚያሰኝ አይመስልም፤ በኋላ ግን ለለመዱት ሰዎች የጽድቅና የሰላም ፍሬ ያስገኝላቸዋል።

12ስለዚህ የዛለውን ክንዳችሁንና የደከመውን ጕልበታችሁን አበርቱ። 13ዐንካሳው እንዲፈወስ እንጂ የባሰውኑ እንዳያነክስ “ለእግራችሁ ቀና መንገድ አብጁ።”

## እግዚአብሔርን ስላለመታዘዝ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

14ከሰው ሁሉ ጋር በሰላም ለመኖር የሚቻላችሁን ሁሉ አድርጉ፤ ለመቀደስም ፈልጉ፤ ያለ ቅድስና ማንም ጌታን ማየት አይችልም፤ 15ከእናንተ ማንም የእግዚአብሔር ጸጋ እንዳይጐድልበት ደግሞም መራራ ሥር በቅሎ ችግር እንዳያስከትልና ብዙዎችን እንዳይበክል ተጠንቀቁ። 16ለአንድ ጊዜ መብል ሲል ብኵርናውን እንደ ሸጠው እንደ ዔሳው ማንም ሴሰኛ ወይም እግዚአብሔርን የማያከብር ሆኖ እንዳይገኝ ተጠንቀቁ። 17በኋላም ይህንኑ በረከት ሊወርስ በፈለገ ጊዜ፣ እንደ ተከለከለ ታውቃላችሁ፤ በረከቱን በእንባ ተግቶ ቢፈልግም መልሶ ሊያገኘው አልቻለም።

18ሊዳሰስ ወደሚችለውና በእሳት ወደሚቃጠለው ተራራ፣ ወደ ጨለማው፣ ወደ

12፥2 መዝ25፥15፤ ማር16፥19፤ፊል2፥8፡9፤ዕብ2፥9፡10፤13፥13
12፥3 ገላ6፥9፤ራእ2፥3
12፥4 ዕብ10፥32-34፤ 13፥13
12፥5 ቍ3
12፥6 መዝ94፥12፤ 119፥75፤ምሳ3፥11፡12፤ ራእ3፥19
12፥7 ዘዳ8፥5፤ 2ሳሙ7፥14፤ ምሳ13፥24
12፥8 1ጴጥ5፥9
12፥9 ዘኍ16፥22፤ 27፥16፤ኢሳ38፥16፤ ራእ22፥6
12፥10 2ጴጥ1፥4
12፥11 ኢሳ32፥17፤ ያዕ3፥17፡18
12፥12 ኢሳ35፥3
12፥13 ምሳ4፥26፤ ገላ6፥1
12፥14 ማቴ5፥8፤ ሮሜ6፥22፤14፥19
12፥15 ዘዳ29፥18፤ ገላ5፥4፤ዕብ3፥12፡4፥1
12፥16 ዘፍ25፥29-34፤ 1ቆሮ6፥18
12፥17 ዘፍ27፥30-40
12፥18 ዘፀ19፥12-22፤ 20፥18፤ዘዳ4፥11

ነበር። *በጽናት እንሩጥ፤* ሐሥ 20፥24፤ 1ቆሮ 9፥24-26፤ ገላ 2፥2፤ 5፥7፤ ፊል 2፥16፤ 2ጢሞ 4፥7 ይመ። እዚህ ላይ የክርስትና ሕይወት የቀረበው እንደ ረጅም ርቀት ሩጫ እንጂ እንደ አጭር ርቀት ሩጫ አይደለም። አንዳንድ የአይሁድ ክርስቲያኖች ከሰደቱ የተነሣ ውድድሩን አቋርጠው ለመውጣት ተፈትነው ነበር።

12፥2 *ኢየሱስን እንመልከት፤* ሯጭ መድረሻ መሥመሩን አትኩሮ እንደሚመለከት ሁሉ፣ እኛም የእምነታችን ግብና ማረፊያ የሆነውን ኢየሱስን አትኩረን መመልከት አለብን (ፊል 3፥13-14)። *ጀማሪና፤* የ2፥10 ማብ ይመ። *ፍጹም አድራጊ፤* እምነታችን የተጀመረው በእርሱ እንደ ሆነ፣ ፍጻሜ የሚያገኘውም በእርሱ ነው፤ የውድድሩ ጀማሪም ሆነ ፈጻሚ እርሱ ነውና እንዲሁም እርሱ ታላቁ ምስክር ነው፤ ምክንያቱም ከእኛ በፊት ሮጦ አሸንፏል። *በፊቱ ስላለው ደስታ፤* የእርሱ ደስታ የእኛ ዘላለማዊ ቤዛነት መፈጸምና በአብ “ቀኝ” መክበሩ ነው። (የ1፥3ማብ ይመ፤ እንዲሁም ከኢሳ 53፥10-12 ጋር ያነጻጽሩ)። *መስቀሉን ታግሦ፤* ፊል 2፥5-8 ይመ። *ውርደት ንቆ፤* እንደ ክርስቶስ ሁሉ እኛም ስለ ወንጌል የምንቀበለው የአሁኑ ጊዜ ውርደት ወደፊት ከምናገኘው ክብር ጋር ሲወዳደር ቦታ የሚሰጠው አይደለም (11፥26፤ ማቴ 5፥10-12፤ ሮሜ። 8፥18፤ 2ቆሮ 4፥17፤ 1ጴጥ 4፥13፤5፥1፤10 ይመ)።

12፥3 *እርሱን ዐስቡ፤* ደቀ መዛሙርቱ እንዲደርስባቸው ከተጠየቀት መከራ ይበልጥ እጅግ ብርቱ መከራ የተቀበለው እርሱ ነው፤ ይህም እኛ ተስፋ እስክንቈርጥ ድረስ ለሚደርስብን ፈተናና ጭንቀት ታላቅ መጽናናት ይሆንልናል። *ተስፋ እንዳትቈርጡ፤* ኢሳ 40፥28-31 ይመ።

12፥4 *ገና ደማችሁን እስከ ማፍሰስ ድረስ አልተቃወማችሁም፤* ምንም እንኳ ቢሰደዱም ንብረታቸውንም ቢዘረፉ (10፥32-34)፣ በእምነታቸው ግን እስከ መሞት አልደረሱም።

12፥5 *የጌታን ቅጣት፤* መከራና ስደት መታየት ያለባቸው፣ እግዚአብሔር የልጆቹን መንፈሳዊ ሕይወት እያረመና እያነጻ የሚያሠለጥንበት ተደርገው ነው።

12፥6 *ይቀጣል፤* ይህን ቃል ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል “ይገርፋል” ማለት ነው። እግዚአብሔር ከስህተታችን ሊመልሰን ይገርፈናል።

12፥7 *እንደ ልጆቹ ይዞአችኋልና፤* እግዚአብሔር ሲቀጣን ልጆቹ ለመሆናችን አንዱ ማስረጃ ነው። የሚቀጣን ተስፋ እንድንቈርጥ ሳይሆን፣ ቅጣቱ የመጽናናትና የመጽናት መሠረት እንዲሆንልን ነው (ቍ 10)።

12፥11 *የጽድቅና የሰላም ፍሬ ያስገኝላቸዋል፤* በፍጹም ታዛዥነት ከተቀበሉት (ቍ 9 ይመ)፣ ቅጣት መልካምና ጠቃሚ ነው።

12፥13 *ቀና መንገድ አብጁ፤* በክርስትና እምነታቸው እንደ ሽባ ለሚሽመደመዱ ሰዎች ዕንቅፋት ከመሆን ይልቅ በመንፈሳዊና በምግባራዊ ሕይወታቸው ይበልጥ ማደግ እንዲችሉ ቀጥተኛ (ንጽሕናና ቅድስና የተሞላበት) ሕይወት በመኖር እንድንረዳቸው የቀረበ ጥሪ ነው።

12፥14 *ያለ ቅድስና ማንም ጌታን ማየት አይችልም፤* ከ1ጴጥ 1፥51-16፤ 1ዮሐ 3፥2-3 ጋር ያነጻጽሩ።

12፥15 *የእግዚአብሔር ጸጋ እንዳይጐድልበት፤* ከእግዚአብሔር ጸጋ “እንዳይጎድል” ወይም የእግዚአብሔርን ጸጋ “ሳይዝ እንዳይቀር” ማለት ነው። ይህን የመሰለው ሁኔታ ሊከሠት እንደሚችል በ2፥1-4፤6፥4-8 ላይ ተገልጾአል። *መራራ ሥር፤* ትዕቢት፣ ጥላቻ፣ ቅናት ወይም በሌሎች ላይ ጕዳት ሊያደርስ የሚችል ማንኛውም ነገር ነው።

12፥16 *ብኵርናውን እንደ ሸጠው እንደ ዔሳው፤* ዘፍ 25፥29-34 ይመ። ዔሳው፣ ለእውነተኛ ፋይዳዎች ትክክለኛ አመለካከት ስላልነበረው ሕይወትን የናቀ ሰው ነበር (ከፊል 3፥18-19 ጋር ያነጻጽሩ)። ከብኵርናው ይልቅ ሆዱን ለሚሞላ ምግብ ትልቅ ቦታ በመስጠቱ “ብኵርናውን አቃለለ” (ዘፍ 25፥34)።

12፥17 *እንደ ተከለከለ፤* ብኵርናውን ስላጣ ዐዘነ እንጂ በኀጢአቱ ንስሓ አልገባም (ዘፍ 27 በተለይም ቍ 41)። ሐዘኑም “ወደ ድነት ለሚያደርስ ንስሓ” የሚያበቃው “እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ የሆነ ሐዘን” ሳይሆን “ለሞት የሚያበቃ ያለማዊ ሐዘን” ነው (2ቆሮ 7፥10)። *በረከቱን፤* የበኵር ልጅ መሆን ነው። የዚህ መልእክት ተደራሲዎች ከደረሰባቸው ስደት እፎይ ለማለት እምነታቸውን ለመጣል ያሰቡ ይመስላል። በዚህ በዓለም ለሚገኝ ጊዜያዊ ደስታ ብለው መንፈሳዊ ብኵርናቸውን ቢሸጡ፣ በክርስቶስ ያላቸውን በረከት ያጣሉ። *በእንባ* ዘፍ 27፥34-38 ይመ።

*12፥18-21፤* እነዚህ ቅሶች በሲና ተራራ ላይ ሕግ ሲሰጥ የነበረውን አስፈሪ ሁኔታ ይገልጻሉ (ዘፀ 19፥10-25፤ ዘዳ 4፥11-

ጭጋጉና ወደ ፀውሎ ነፋሱ አልደረሳችሁም፤ 19ወደ መለከት ድምፅ፣ ወይም ቃልን ወደሚያሰማ ድምፅ አልመጣችሁም፤ የሰሙትም ሌላ ቃል ተጨምሮ እንዳይናገራቸው ለመኑ:: 20ምክንያቱም "እንስሳ እንኳ ተራራውን ቢነካ፣ በድንጋይ ተወግሮ ይሙት" የሚለውን ትእዛዝ መሸከም አልቻሉም:: 21በዚያ ይታይ የነበረውም ሁኔታ እጅግ አስፈሪ ነበርና፣ ሙሴ "በፍርሀት ተንቀጠቀጥሁ" አለ::

22እናንተ ግን ወደ ጽዮን ተራራ፣ ወደ ሰማያዊት ኢየሩሳሌም፣ ወደ ሕያው እግዚአብሔር ከተማ መጥታችኋል፤ በደስታ ወደ ተሰበሰቡት ወደ አእላፋት መላእክት፣ 23ስማቸው በሰማይ ወደ ተጻፈው ወደ በኵራት ማኅበር ቀርባችኋል፤ የሁሉ ዳኛ ወደ ሆነው ወደ እግዚአብሔር፣ ፍጹምነትን ወዳገኙት ወደ ጻድቃን መንፈሶች፣ 24የአዲስ ኪዳን መካከለኛ ወደ ሆነው ወደ ኢየሱስ፣ እንዲሁም ከአቤል ደም የተሻለ ቃል ወደሚናገረው ወደ ተረጨው ደም ደርሳችኋል::

25የሚናገረውን እርሱን እምቢ እንዳትሉት ተጠንቀቁ:: እነዚያ ከምድር ሆኖ ሲያስጠነቅቃቸው የነበረውን እምቢ ባሉ ጊዜ ካላመለጡ፣ እኛ ከሰማይ የመጣው ሲያስጠነቅቀን ከእርሱ ብንርቅ እንዴት ልናመልጥ እንችላለን? 26በዚያን ጊዜ ድምፁ ያናወጠው ምድርን ነበር፤ አሁን ግን፣ "ምድርን ብቻ ሳይሆን፣ ሰማያትንም አንድ ጊዜ ደግሜ እናውጣለሁ" ብሎ ቃል ገብቶአል:: 27አንድ ጊዜ "ደግሜ" የሚለው ቃል የሚያመለክተው የማይናወጡት ጸንተው ይኖሩ ዘንድ፣ የሚናወጡት ይኸውም የተፈጠሩት የሚወገዱ መሆናቸውን ነው::

28ስለዚህ ከቶ የማይናወጥ መንግሥት ስለ ምንቀበል እግዚአብሔርን እናመስግን፤ ደግሞም ደስ በሚያሰኘው መንገድ በአክብሮትና በፍርሀት እናምልከው፤ 29አምላካችን የሚያጠፋ እሳት ነውና::

### የመጨረሻ ምክር

**13** እርስ በርሳችሁ እንደ ወንድማማች ተዋደዱ:: 2እንግዶችን መቀበል አትርሱ፤ አንዳንዶች ይህን ሲያደርጉ፣ ሳያውቁ መላእክትን አስተናግደዋልና:: 3በእስር ላይ ያሉትን ከእነርሱ ጋር እንደ ታሰራችሁ ሆናችሁ ዐስቡአቸው፤ እንዲሁም በሰው እጅ የሚንገላቱትን ራሳችሁ መከራ እንደምትቀበሉ አድርጋችሁ ዐስቡአቸው::

4ጋብቻ በሁሉም ዘንድ ይከበር፤ መኝታውም ንጹሕ ይሁን፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር በአመንዝሮችና በሴሰኞች ሁሉ ላይ ይፈርዳል:: 5ራሳችሁን ከፍቅረ ንዋይ ጠብቁ፤ ባላችሁ ነገር ረክታችሁ ኑሩ፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር፣

"ከቶ አልተውህም፤
በፍጹም አልጥልህም" ብሎአል::
6ስለዚህ በሙሉ ልብ፣
"ጌታ ረዳቴ ነው፤ አልፈራም፤

12፥19 ዘፀ20፥18: 19፤ዘዳ4፥12፤5፥5:25፤ 18፥16
12፥20 ዘፀ19፥12: 13
12፥21 ዘዳ9፥19
12፥22 ኢሳ24፥23፤ 60፥14፤ማቴ16፥16፤ ገላ4፥26፤ ዕብ11፥10፤ 13፥14፤ራእ14፥1
12፥23 ዘፍ18፥25፤ ዘፀ4፥22፤መዝ94፥2፤ ፊል3፥12፤ራእ20፥12
12፥24 ዘፍ4፥10፤ ገላ3፥20፤ዕብ9፥19፤ 10፥22፤11፥4፤1ጴጥ1፥2
12፥25 ዘዳ18፥19፤ ዕብ1፥1፤2፥2:3፤ 3፥12፤8፥5፤10፥29፤ 11፥7
12፥26 ዘፀ9፥18፤ ሐጌ2፥6
12፥27 ኢሳ34፥4፤ 54፥10፤1ቆሮ7፥31፤ ዕብ1፥11:12፤ 2ጴጥ3፥10፤1ዮሐ2፥17
12፥28 መዝ15፥5፤ ዳን2፥44፤ሚል2፥5፤ 4፥2፤ዕብ13፥15
12፥29 ዘፀ24፥17፤ ዘዳ4፥24፤9፥3፤ መዝ97፥3፤ ኢሳ33፥14፤2ተሰ1፥7
13፥1 ሮሜ12፥10
13፥2 ዘፍ18፥1-33፤ 19፥1-3፤ኢዮ31፥32፤ ማቴ25፥35፤ ሮሜ12፥13
13፥3 ማቴ25፥36፤ ቈላ4፥18፤ዕብ10፥34
13፥4 ዘዳ22፥22፤ ሚል2፥15፤1ቆሮ6፥9፤ 7፥38፤1ጢሞ4፥3፤ ራእ22፥15
13፥5 ዘዳ31፥6:8፤ ኢሱ1፥5፤ፊል4፥11፤ 1ጢሞ3፥3፤6፥6:8
13፥6 መዝ118፥6:8

12፤ 5፥22-26 ይመ):: ዝርዝር ሐሳቡ የሚያተኩረው በብሉይ ኪዳን ተራራ፣ ሥርዐት፣ አስፈሪ ማስጠንቀቂያዎችና ከባድ ቅጣቶች ላይ ነው:: በኢየሱስ ክርስቶስ የሚያምኑ ግን እንዲህ ዐይነት የሚያስፈራ ኪዳን ስለሌላቸው፣ ወደ ብሉይ ኪዳኑ ሥርዐት ለመመለስ ማሰብ አይገባቸውም::

12፥22 *ጽዮን ተራራ፤* በኢየሩሳሌም ወይም በደቡብ ምሥራቅ ክፍል የምትገኘውን የጽዮን ተራራ ሳይሆን፣ ሰማያዊቷን የእግዚአብሔር ከተማና ከእርሱም ጋር በዚያ የሚኖሩትን ነው (11፥10:13-16፤13፥14፤ ፊል 3፥20 ይመ):: ብሉይ ኪዳን የተሰጠበት ሁኔታና (ቊ 18-21) የአዲስ ኪዳንን ልዩ ባሕርይ (ቊ 22-24)፣ በሁለቱ ኪዳኖች መካከል መሠረታዊ ልዩነት ያለ መሆኑን ከማመልከቱም በላይ፣ ወደ አይሁድ እምነት ለመመለስ የሚያስቡትን ብርቱ ማስጠንቀቂያና ማሳሰቢያ ይሰጣቸዋል:: *ወደ … አእላፋት መላእክት፤* ራእ 5፥11-12 ይመ::

12፥23 *በኵራት ማኅበር፤* በጥቅሉ የቤተ ክርስቲያን አካል የሆኑትን አማኞች ነው፤ (1) ቀደም ሲል በቍጥር 22 ላይ ስለተጠቀሱ፣ መላእክቱን ሊሆን አይችልም፤ (2) ምንም እንኳ ክርስቶስ በኩር ተብሎ ቢጠራም (1፥6፤ ሮሜ 8፥29፤ ቈላ 1፥15-18፤ ራእ 1፥5) በዚህ ቁጥር ላይ "በኵራት" የሚለው ቃል እርሱን አያመለክትም፤ ምክንያቱም የግሪኩ ቃል ብዙ ቍጥር ነው፤ (3) ስማቸው በሰማይ ስለተመዘገበ የተቤዡ መሆናቸውን ያመለክታል (ራእ 3፥5፤ 13፥8፤ 17፥8፤ 20፥12፤ 21፥27 ይመ):: በኵራት የሚለው ስያሜ የሚያመለክተው ልጂቁ በኵርና "ሁሉን ወራሽ" (ዕብ 1፥2) ከሆነው ከክርስቶስ ጋር አብረው ወራሾች መሆናቸውን ነው:: *የሁሉ ዳኛ ወደ ሆነው ወደ እግዚአብሔር፤* 4፥13፤ ሮሜ 14፥10-12፤ 1ቆሮ 3፥10-15፤ 2ቆሮ 5፥10፤ ራእ 20፥11-15 ይመ:: *ፍጹምነትን ወዳገኙት ወደ ጻድቃን መንፈሶች፤* በአብዛኛው ከክርስትና እምነት በፊት የነበሩትን እንደ አቤልና (11፥4) ኖኅ (11፥7) የመሳሰሉ አማኞችን ነው:: እነዚህ ሰዎች "መንፈሶች" የተባሉት ትንሣኤን ስለሚጠባበቁ ሲሆን፣ ጻድቃን የተባሉት ደግሞ እግዚአብሔር የአብርሃምን እምነት ጽድቅ አድርጎ እንደ ቈጠረለት ሁሉ የእነርሱንም እምነት ጽድቅ አድርጎ ስለ ቈጠረላቸው ነው(ሮሜ 4፥3 ይመ):: ይሁን እንጂ ክርስቶስ በመስቀል ላይ ሞቶ ፍጹም እስኪያደርገው ድረስ እውነተኛ ጽድቅ አይኖርም (11፥40፤ ሮሜ 3፥24-26፤ 4፥23-25 ይመ)::

12፥24 *የአዲስ ኪዳን መካከለኛ፤* የ7፥22፤ 8፥6 እና ማብራሪያውን እንዲሁም 8፥13፤ 9፥15፤ 1ጢሞ 2፥5 ይመ:: *ከአቤል ደም የተሻለ ቃል ወደሚናገረው፤* የአቤል ደም ስለ ፍትሕና ስለ ፍርድ ሲጮኽ (የዘፍ 4፥10 ማብ ይመ)፣ በመስቀል ላይ የፈሰሰው የክርስቶስ ኢየሱስ ደም ግን ስለ ይቅርታና ስለ ዕርቅ ይጮኻል (9፥12፤ 10፥9፤ ቈላ 1፥20፤ 1ዮሐ 1፥7)::

12፥25 *የሚናገረውን፤* እግዚአብሔርን ነው:: *ከምድር ሆኖ ሲያስጠነቅቃቸው* በሲና ተራራ ነው:: *ከሰማይ የመጣው ሲያስጠነቅቀን፤* ክርስቶስ ከሰማይም የሰማይም ነው (1፥1-3፤ 4፥14፤ 6፥20፤ 7፥26፤ 9፥24):: የተቀበልነው ታላቅ መገለጥ በመሆኑ ትልቅ ኀላፊነት አለብን፤ ስለዚህም ትልቅ ጥንቃቄ ማድረግ ያስፈልገናል (2፥2-4)::

12፥26 *ያናወጠው ምድርን ነበር፤* ዘፀ 19፥18፤ መሳ 5፥5፤ መዝ 68፥7-8 ይመ::

12፥27 *ደግሜ፤* ክርስቶስ ዳግም ተመልሶ ሲመጣ ታላቅ ነውጥ ይሆናል:: *የማይናወጡት፤* የሚመጣውን መንግሥት ነው (ቊ 28)::

12፥28 *ደስ በሚያሰኘው መንገድ…እናምልከው፤* ዮሐ 4፥19-24፤ ሮሜ 12፥1 ይመ::

*12፥29፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ:: ከዘፀ24፥17፤ ዘዳ9፥3 ጋር ያነጻጽሩ::

13፥2 *ሳያውቁ መላእክትን አስተናግደዋልና፤* ይህም አብርሃም (ዘፍ 8)፣ ጌዴዎን (መሳ 6) እንዲሁም ማኑሄ (መሳ 13) እንዳደረጉት ነው::

13፥3 *በእስር ላይ ያሉትን…እንዲሁም በሰው እጅ የሚንገላቱትን …ዐስቡአቸው፤* 10፥32-34፤ 1ቆሮ 12፥26 ይመ::

13፥5፤ *ከፍቅረ ንዋይ፤* ሉቃ 12፥15:21፤ ፊል4፥10-13፤ 1ጢሞ6፥6-10: 17፥19 ይመ:: *ረክታችሁ ኑሩ፤* ፊል4፥11-12፤1ጢሞ6፥8 ይመ::

ሰው ምን ሊያደርገኝ ይችላል?" እንላለን።

[7]የእግዚአብሔርን ቃል የነገሯችሁን መሪዎቻችሁን ዐስቡ፤ የኑሮአቸውን ፍሬ ተመልከቱ፤ በእምነታቸውም ምሰሉአቸው። [8]ኢየሱስ ክርስቶስ ትናንትና፣ ዛሬም ለዘላለምም ያው ነው።

[9]በልዩ ልዩ ዐይነት እንግዳ ትምህርቶች አትወሰዱ፤ ልባችን የሚጸናው በጸጋ እንጂ የምግብ ሥርዐት በመጠበቅ አይደለም፤ ይህንን ሥርዐት የሚጠብቁት እንኳ በዚህ አልተጠቀሙም። [10]በድንኳኒቱም የሚያገለግሉ ከዚያ ሊበሉ መብት ያላገኙበት መሠዊያ አለን።

[11]ሊቀ ካህናቱ ስለ ኀጢአት ስርየት የሚሆነውን የእንስሳት ደም ይዞ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ይገባል፤ የእንስሳቱ ሥጋ ግን ከሰፈር ውጭ ይቃጠላል። [12]እንዲሁም ኢየሱስ በራሱ ደም አማካይነት ሕዝቡን ሊቀድስ ከከተማው በር ውጭ መከራን ተቀበለ። [13]ስለዚህ እኛም እርሱ የተሸከመውን ውርደት ተሸክመን ከሰፈር ውጭ ወደ እርሱ እንውጣ። [14]ምክንያቱም በዚህ ቋሚ ከተማ የለንም፤ ነገር ግን ወደፊት የምትመጣዋን ከተማ እንጠብቃለን።

[15]ስለዚህ ዘወትር የምስጋናን መሥዋዕት ይኸውም ለስሙ የሚመሰክሩ የከንፈሮችን ፍሬ በኢየሱስ አማካይነት ለእግዚአብሔር እናቅርብ። [16]ደግሞም መልካም ማድረግንና ያላችሁንም ከሌሎች ጋር መካፈልን አትርሱ፤ እግዚአብሔር ደስ የሚሰኘው እንደዚህ ባለው መሥዋዕት ነውና።

[17]ለመሪዎቻችሁ ታዘዙ፤ ተገዙላቸውም። ምክንያቱም እነርሱ በብርቱ የሚያስጠይቃቸው ነገር ስላለባቸው፣ ስለ ነፍሳችሁ ጒዳይ ይተጋሉ። ስለዚህ ሥራቸውን በሐዘን ሳይሆን በደስታ ማከናወን እንዲችሉ ታዘዟቸው። አለበለዚያ አይበጃችሁም።

[18]ለእኛ ደግሞ ጸልዩልን። በሁሉም መንገድ በመልካም አኗኗር ለመኖር የሚናፍቅ ንጹሕ ኅሊና እንዳለን እርግጠኞች ነን። [19]በተለይም ወደ እናንተ በፍጥነት ተመልሼ እንድመጣ ትጸልዩልኝ ዘንድ ዐደራ እላችኋለሁ።

[20]በዘላለም ኪዳን ደም የበጎች ታላቅ እረኛ የሆነውን ጌታችን ኢየሱስን ከሞት ያስነሣው የሰላም አምላክ፣ [21]ፈቃዱን እንድታደርጉ በመልካም ነገር ሁሉ ያስታጥቃችሁ፤ ደስ የሚያሰኘውንም በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል በእኛ ያድርግ፤ ለእርሱ እስከ ዘላለም ድረስ ክብር ይሁን፤ አሜን።

[22]ወንድሞች ሆይ፤ የጻፍሁላችሁ መልእክት አጭር እንደ መሆኑ፣ የምክር ቃሌን በትዕግሥት እንድትቀበሉ ዐደራ እላችኋለሁ።

13፥7 ቍ17:24፤ 1ቆሮ16፥16፤ ዕብ4፥12፤6፥12
13፥8 መዝ102፥27፤ ዕብ1፥12
13፥9 ኤፌ4፥14፤ ቈላ2፥7:16፤ዕብ9፥10
13፥10 1ቆሮ9፥13፤ 10፥18፤ዕብ8፥5
13፥11 ዘፀ29፥14፤ ዘሌ4፥12:21፤9፥11፤ 16፥15:27
13፥12 ዮሐ19፥17፤ ሮሜ3፥25፤ኤፌ5፥26
13፥13 ሉቃ9፥23፤ ዕብ11፥26
13፥14 ፊል3፥20፤ ዕብ11፥10:27፤ 12፥22:27
13፥15 ኢሳ57፥19፤ ሆሴ14፥2፤1ጴጥ2፥5
13፥16 ሮሜ12፥13፤ ፊል4፥18
13፥17 ቍ7:24፤ ኢሳ62፥6፤ሐሥ20፥28
13፥18 ሐሥ23፥1፤ 1ተሰ5፥25
13፥19 ፊሞ22
13፥20 ዘፍ9፥16፤ 17፥7:13:19፤ ኢሳ55፥3፤61፥8፤ ሕዝ37፥26፤ ማቴ26፥28፤ ዮሐ10፥11፤ሐሥ2፥24፤ ሮሜ15፥33
13፥21 ሮሜ11፥36፤ 2ቆሮ9፥8፤ፊል2፥13፤1ዮሐ3፥22
13፥22 1ጴጥ5፥12

13፥7 *የእግዚአብሔርን ቃል የነገሯችሁን መሪዎቻችሁን*፤ 2፥3፤ 5፥12 ይመ። *የኑሮአቸውን ፍሬ ተመልከቱ*፤ ምናልባት ይህ የሚያመለክተው እነዚህ ምሳሌያዊ ሕይወት የኖሩ መሪዎች ሞተው ሊሆን ይችላል። *በእምነታቸውም ምሰሉአቸው*፤ 6፥12፤ 1ቆሮ 4፥16፤ ኤፌ 5፥1፤ 1ተሰ 1፥6-7፤ 2፥14፤ 3ዮሐ 11 ይመ።

13፥8 *ኢየሱስ ክርስቶስ...ያው ነው*፤ ክርስቶስ ከቶ እንደማይለወጥ የሚያሳይ ሲሆን፣ ከፍ ሲል ከሚገኘው ቍጥር ጋር እንደሚያያዝ ምንም ጥርጥር የለውም። የቀደሙት መሪዎቻቸው እምነት የተመሠረተው መቼም በማይለወጠው ክርስቶስ ላይ ነው። *ትናንትና*፤ ምናልባት ክርስቶስ በዚህ ምድር በነበረበት ጊዜ የዐይን ምስክሮች እርሱን ያዩበት ጊዜ ይሆናል (2፥3)። *ዛሬም*፤ የዐይን ምስክሮች ያዩት ክርስቶስ ዛሬም ያው ነው፤ ስለ እርሱም የተናገሩት ሁሉ እውነት ነው። *ለዘላለምም*፤ ሁልጊዜ የሚኖረው በዚህ ዐይነት ነው። የክርስቶስን ፍጹም ሉዓላዊነት እንደ ተራ ነገር በመቍጠር ከእርሱ እጅግ ወደሚያንሰው ወደ አሮን ሥርዐተ ክህነትና ወደ መሥዋዕቱም መመለስ (ምዕ 5-10 ይመ) ማለት ወንጌልን መናቅ ማለት ነው።

13፥9 *የምግብ ሥርዐት*፤ የአይሁድ የሕግ መምህራን እንደሚሉት ነው። የቀድሞው የሙሴ ሥርዐት ክርስቶስ በመስቀል ላይ በሞተ ጊዜ ተሽሯል፤ ስለዚህ ዳግመኛ እንዲያንሰራራ መደረግ የለበትም።

13፥10 *መሠዊያ አለን*፤ የአሮን ሥርዐተ ክህነት መወገዱንና ክርስቶስ ልዩና ብቸኛ ካህን በሆነበት በመልከ ጼዴቅ ሥርዐተ ክህነት መተካቱን ለማመልከት ይሆናል። *ሊበሉ መብት ያላገኙበት*፤ በስርየት ቀን ካህናቱ ከመሥዋዕቱ መብላት አይችሉም፤ እኛ ግን ከመሥዋዕቱ መካፈል እንችላለን፤ የምንካፈለውም በመንፈስ ክርስቶስን በእምነት በመቀበል ነው (ዮሐ 6፥48-58 ይመ)። በብሉይ ኪዳን ሥር ከነበሩት ካህናት ይልቅ እኛ እጅግ የሚበልጥ መብት አለን።

13፥11 *ከሰፈር ውጭ ይቃጠላል*፤ ዘሌ 4፥12 እና ማብራሪያውን እንዲሁም፣ 16፥17 ይመ።

13፥12 *እንዲሁም ኢየሱስ...ከከተማው በር ውጭ መከራን ተቀበለ*፤ ክርስቶስ ከኢየሩሳሌም ውጭ መሞቱ የሕዝቡ ኀጢአት መወገዱን ያሳያል፤ ለመሥዋዕት የሚቀርበው የእንስሳት አካል ከእስራኤል ሰፈር ውጭ ይጣል ነበር።

13፥13 *ከሰፈር ውጭ ወደ እርሱ እንውጣ*፤ ከይሁዲነት ወደ ክርስቶስ ዘወር እንዲሉ የቀረበ ጥሪ ነው። እርሱ ከከተማው ውጭ በውርደት እንደ ሞተ፣ የዚህ መልእክት ተደራሲዎችም ከይሁዲነት ወደ ክርስቶስ ዘወር ሲሉ ውርደትን ለመቀበል ፈቃደኞች መሆን አለባቸው።

13፥14 *የምትመጣዋን ከተማ*፤ የ11፥10:14:16 ማስታወሻ ይመ።

13፥15 *የምስጋናን መሥዋዕት*፤ እዚህ ላይ "መሥዋዕት" የሚለው ቃል ተምሳሌታዊ በሆነ አገላለጽ የገባው ለእግዚአብሔር የሚቀርበውን ስጦታ ለማመልከት ነው (ሮሜ 12፥1፤ ፊል 4፥18 ይመ)። እንስሳትን መሥዋዕት አድርጎ ማቅረብ ፍጹም ቀርቶአል።

13፥17 *ለመሪዎቻችሁ*፤ በቍጥር 7 ላይ የተጠቀሱትንና የሞቱትን ሳይሆን፣ አሁን በሕወት ያሉትን መሪዎቻቸውን ነው። *ተገዙላቸውም*፤ ጸሓፊው እንዲህ ሲል ለፈላጭ ቈራጭ አመራር ቦታ መስጠቱ አይደለም (3ዮሐ 9-10 ይመ)፤ በመላው አዲስ ኪዳን ውስጥ ባለሥልጣኖችን ማክበር፣ በቤተ ክርስቲያንም ውስጥ ሥርዐትን ማስፈን ተገቢ እንደ ሆነ ትምህርት ተሰጥቶአል።

13፥19 *ወደ እናንተ በፍጥነት ተመልሼ እንድመጣ*፤ የዚህ መልእክት ጸሓፊ ማን እንደ ሆነና የትስ ሆኖ እንደሚጽፍ በውል ባይታወቅም፣ "ተመልሼ እንድመጣ" የሚለው ሐረግ ተደራሲዎቹን ለመጎብኘት ፈልጎ ምናልባት በአገልግሎቱ ምክንያት የዘገየ መሆኑን ያመለክታል። እስር ቤት እንዳልሆነ ግን ከቍ 23 በግልጽ መረዳት ይቻላል።

*13፥20-21*፤ ይህ ቃለ ቡራኬ ለመልእክቱ ተገቢ መደምደሚያ ነው። *የሰላም አምላክ*፤ በቃለ ቡራኬ ጊዜ ለእግዚአብሔር የሚውል አገላለጽ ነው (ሮሜ 15፥33፤ 16፥20፤ ፊል 4፥9፤ 1ተሰ 5፥23 ይመ)።

13፥20 *በዘላለም ኪዳን*፤ አዲሱን ኪዳን ነው (የ8፥8-12 ማብ ይመ)። ኤርምያስ በ31፥31 ላይ አዲሱ ኪዳን በማለት የጠራውን፣ በ32፥40 ላይ የዘላለም ኪዳን በማለት ይገልጸዋል (ኢሳ 55፥3 እና ማብራሪያውን እንዲሁም፤ 61፥8 ይመ)። ስለ ኪዳኑ ደም በተመለከተ የ10፥29 ማብ ይመ። *ታላቅ እረኛ*፤ ለምሳሌ መዝ 23፤ ኢሳ 40፥11፤ ሕዝ 34፥11-16፤ 23፤ 37፥24፤ ዮሐ 10፥2-3፤ 11፤ 14፤ 27፤ 1ጴጥ 2፥25፤ 5፥4 ይመ።

*13፥22-25*፤ በስተመጨረሻ እንደ አዲስ ማሳሰቢያ የተሰጠ ክፍል ነው።

13፥22 *አጭር*፤ መልእክቱን አጭር የሚያሰኘው ክርስቶስ ከሁሉ የሚበልጥ መሆኑን ከዚህ በላይ መግለጽ ሲቻል፣ ከብዙ በጥቂቱ ብቻ የቀረበ በመሆኑ ነው።*የምክር ቃሌን*፤ የመልእክቱ

[23]ወንድማችን ጢሞቴዎስ እንደተፈታ ታውቁ ዘንድ እፈልጋለሁ፤ ቶሎ ከመጣ፣ ከእርሱ ጋር ሳያችሁ እመጣለሁ።

13፥23 ሐሥ16፥1

13፥24 ቁ.7፡17፤ ሐሥ18፥2

13፥25 ቈላ4፥18

[24]ለመሪዎቻችሁ ሁሉና ለቅዱሳን ሁሉ ሰላምታ አቅርቡልኝ። ከኢጣሊያ የሆኑትም ሰላምታ ያቀርቡላችኋል።

[25]ጸጋ ከሁላችሁ ጋር ይሁን።

ፍሬ ሐሳብ አማኞች በክርስትና ሕይወታቸው እየጎለበቱና እየበሰሉ እንዲሄዱ፣ ከክርስቶስም ተለይተው እንዳይወድቁ የሚያሳስብ ነው።

13፥23 *ጢሞቴዎስ እንደተፈታ*፣ የመልእክቱ ተደራሲዎች በሚገባ የሚያውቁት ጢሞቴዎስ ከእስር ቤት የተፈታው በቅርቡ ነው።

13፥24 *ለመሪዎቻችሁ*፤ በቁ.17 ላይ ተጠቅሰዋል። *ከኢጣሊያ የሆኑትም*፣ ይህ መልእክት የተጻፈው ከኢጣሊያ ወይም ለኢጣሊያ ሰዎች ነው ማለት አይደለም። ጸሓፊው በኢጣሊያ ለሚገኙ አማኞች ሰላምታውን እያስተላለፈ ነው።

# የያዕቆብ መልእክት

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ጸሐፊው ራሱ ያዕቆብ እንደ ሆነ ገልጿል (1፥1)፤ እርሱም የጌታ ወንድም እና በሐዋርያት ሥራ ም 5 ላይ ለተጠቀሰው ጉባኤ መሪ ሳይሆን አይቀርም። በአዲስ ኪዳን ውስጥ አራት ሰዎች በዚህ ስም ተጠርተዋል። ሐዋርያው ያዕቆብ የመጀመሪያው ሰማዕት ሆኖ በ44 ዓ.ም. ስለተሠዋ፣ የዚህ መልእክት ጸሐፊ እርሱ ሊሆን አይችልም። "ያዕቆብ" በሚል ስም የተጠሩ ሌሎች ሁለት ሰዎች አሉ፤ ሆኖም እነርሱ እንዳልጻፉት ግልጽ ነው። በማቴ 13፥55 ላይ ከኢየሱስ ወንድሞች ስም ዝርዝር ውስጥ በመጀመሪያ የተጠቀሰው ያዕቆብ ከወንድሞቹ ሁሉ እርሱ ታላቅ ሳይሆን አይቀርም። ያዕቆብ በመጀመሪያ በጌታ አላመነም ነበር፣ ስለዚህም የተግጻሮት ሐሳብ በኢየሱስ ላይ ይሰነዝር ነበር (ዮሐ 7፥2-5)። በኋላ ግን በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የላቀ ሞገስ ያለው ሰው ሆነ፤ ስለዚህም:-

1) ጌታ ኢየሱስ ከትንሣኤ በኋላ ራሱን ከገለጠላቸው ጥቂት ደቀ መዛሙርት መካከል እነሆ እርሱ አንዱ ነው (1ቆሮ 15፥7)፤

(2) ጳውሎስ የቤተ ክርስቲያን "ዐምድ" በማለት ጠቅሶታል (ገላ 2፥9)።

(3) ጳውሎስ ክርስቶስን አምኖ ከተለወጠ በኋላ በኢየሩሳሌም የመጀመሪያ ጉብኝቱን ሲያደርግ ከያዕቆብ ጋር ተገናኝቶአል (ገላ 1፥19)።

(4) ጳውሎስ ለመጨረሻ ጊዜ ኢየሩሳሌምን በጐበኘበት ጊዜም እንዲሁ ከያዕቆብ ጋር ተገናኝቶአል (ሐሥ 21፥18)።

(5) ጴጥሮስ ከእስር ቤት እንደወጣ ለያዕቆብ እንዲነገረው አሳስቦ ነበር (ሐሥ 12፥17)፤

(6) በኢየሩሳሌም ዐቢይ ጉባኤ ላይ ያዕቆብ መሪ ነበር (ሐሥ 15፥13)።

(7) ይሁዳ በመልእክቱ ውስጥ ማንነቱን የገለጸው፣ "የያዕቆብ ወንድም" (ይሁዳ 1፥1) በማለት ነው፤

ከዚህ እንደምንረዳው ያዕቆብ እጅግ ታዋቂ ሰው እንደ ነበረ ነው። ይኸው ያዕቆብ በሰማዕትነት ሕይወቱ ያለፈው በ62 ዓ.ም. ገደማ ነበር።

### መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ

አንዳንዶች ይህ መልእክት የተጻፈው በ60 ዓ.ም. መግቢያ ላይ ነው ይላሉ፤ ይሁን እንጂ ከ50 ዓ.ም. በፊት የተጻፈ ስለ መሆኑ አንዳንድ ምልክቶች ያስገነዝባሉ፤

1. መልእክቱ የአይሁድን አስተሳሰብ ይዞ በመገኘቱ በቤተ ክርስቲያኒቱ አይሁድ ምእመናን በብዛት በሚገኙበት ወቅት የተጻፈ ነው።

2. በቤተ ክርስቲያኒቱ የሚገኙት ኀላፊዎችም "ሽማግሌዎችና" (15፥14) "አስተማሪዎች" (3፥1) ብቻ ነበሩ።

3. አሕዛብ መገረዝ አለባቸው የሚል ክርክር አልተነሣም ነበር፤

4. በግሪክ "ምኵራብ" የሚለው ቃል የክርስቲያኖችን ስብሰባ ለማመልከት (2፥2) ጥቅም ላይ መዋሉ ይህ መልእክት የተጻፈበትን ጊዜ በትክክል ያመለክታል፣ ይኸውም መልእክቱ ከአዲስ መጻሕፍት ሁሉ ቀዳሚ ሆኖ የተጻፈ ነው፤ ምናልባት ከዚህ መልእክት በፊት የተጻፈ አለ ከተባለ ወደ ገላትያ ሰዎች የተጻፈው መልእክት ብቻ ነው።

### ተደራስያኑ

የዚህ መልእክት ተደራስያን እነማን እንደ ሆኑ በግልጽ የምናገኘው በ1፥1 ላይ ነው፤ ይኸውም "በአሕዛብ መካከል ተበትነው ለሚገኙት አሥራ ሁለት ነገዶች" የሚል ነው። አንዳንዶች ይህ አባባል በአጠቃላይ ክርስቲያኖችን ያመለክታል ቢሉም ፣ "ለአሥራ ሁለቱ ነገዶች" የሚለው ስያሜ በይበልጥ የሚያመለክተው የአይሁድ ክርስቲያኖችን ነው። ከዚህም በላይ መልእክቱ የአይሁድን የአገላለጽ ስልት ይዞ የሚጓዝ ስለ ሆነ ተደራስያኑ አይሁድ መሆናቸው ግልጽ ነው (በ5፥4 ላይ "የሠራዊት ጌታ እግዚአብሔር" የሚለው አይሁድ እግዚአብሔርን ለመጥራት የሚጠቀሙበት የማዕረግ ስም ተደራስያኑ ያለ ጥርጥር አይሁድ መሆናቸውን የሚያመለክት ነው)። የዚህ መልእክት ተደራስያን ክርስቲያኖች ለመሆናቸውም ከ2፥1፤ 5፥7-8 መረዳት ይቻላል። እነዚህ ክርስቲያኖች የመጀመሪያዎቹ የኢየሩሳሌም ክርስቲያኖች እንደ ነበሩ ይገመታል፤ እነርሱም እስጢፋኖስ በሰማዕትነት ከሞተ በኋላ በፊንቄ፣ በቆጵሮስና በሶርያዋ አንጾኪያ ተበትነው ይገኙ ነበር (ሐሥ 8፥1፤11፥19)። ያዕቆብ ስለ ፈተናና ስለ ጭቆና ማውሳቱ ተደራስያኑ በቅርብ የሚያውቃቸው የኢየሩሳሌም ምእመናን መሆናቸውን የሚያመለክት ነው። ያዕቆብ የኢየሩሳሌም ቤተ ክርስቲያን መሪ እንደ መሆኑ፣ የተበተኑትንና በጭንቀት ላይ የሚገኙትን ምእመናን ለማስተማርና ለማጽናናት፣ የመጋቢነት ተግባሩን በጽሑፍ ሲያከናውን ይታያል።

**የመልእክቱ ልዩ ባሕርይ**

ይህን መልእክት ልዩ የሚያደርጉት ባሕርያት የሚከተሉት ናቸው፤

(1) የማያጠራጥር ግልጽ የሆነ አይሁዳዊ ገጽታው፣ (2) ሕያው በሆነው የክርስትና ሕይወት ላይ አጽንኦት ማድረጉ፤ ይህም የክርስትና ሕይወት በበጎ ሥራ የሚገለጽ ነው ማለቱ፣ (3) ቅልብጭ ያለው መዋቅሩ፣ (4) ከኢየሱስ የተራራ ስብከት ጋር ያለው ተጓዳኝነት (2፥5ን ከማቴ 5፥3፤3፥10-12ን ከ ማቴ 5፥12ን ከማቴ5፥15-20፤ 5፥12ን ከማቴ5፥33-37 ጋር ያነጻጽሩ)፣ (5) መጽሐፈ ምሳሌን ከመሳሰሉ የብሉይ ኪዳን የጥበብ መጻሕፍት ጋር ተመሳሳይ መሆኑና፣ (6) መልእክቱ የተጻፈበት የግሪክ ቋንቋ አጠቃቀም በጣም ግሩም መሆኑ ናቸው::

**አስተዋፅኦ**

1. ሰላምታ (1፥1)
2. ፈተናና መከራ (1፥2-18)
   ሀ. የእምነት መፈተን (1፥2-12)
   ለ. የመከራ መንሥኤ (1፥13-18)
3. መስማትና ማድረግ (1፥19-27)
4. አድልዎ መወገዙ (2፥1-13)
5. እምነትና ሥራ (2፥14-26)
6. አንደበትን መግዛት (3፥1-12)
7. ሁለት ዐይነት ጥበብ (3፥13-18)
8. ዓለማዊነትን በተመለከተ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ (ም 4)
   ሀ. ጠበኝነት (4፥1-3)
   ለ. በመንፈሳዊ ረገድ ታማኝ ሆኖ አለመገኘት (4፥4)
   ሐ. ትዕቢት (4፥5-10)
   መ. ሐሜተኝነት (4፥11-12)
   ሠ. ጉረኝነት (4፥13-17)
9. ለጨቋኝ ባለ ጠጎች የተሰጠ ማስጠንቀቂያ (5፥1-6)
10. ልዩ ልዩ ምክሮች (5፥7-20)
    ሀ. በመከራ ስለ መታገሥ (5፥7-11)
    ለ. ስለ መሐላ (5፥12)
    ሐ. በእምነት ስለሚደረግ ጸሎት (5፥13-18)
    መ. ከእውነት ስላፈገፈጉ ሰዎች (5፥19-20)

1 የእግዚአብሔርና የጌታ የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋይ የሆነው ያዕቆብ፤ ለዐሥራ ሁለቱ ነገዶች፤

ሰላም ለእናንተ ይሁን::

## መከራና ፈተና

[2]ወንድሞቼ ሆይ፤ ልዩ ልዩ መከራ ሲደርስባችሁ እንደ ሙሉ ደስታ ቍጠሩት [3]ምክንያቱም የእምነታችሁ መፈተን ትዕግሥትን እንደሚያስገኝ ታውቃላችሁ:: [4]ምንም የማይጐድላችሁ ፍጹማንና ምሉኣን እንድትሆኑ ትዕግሥት ሥራውን ይፈጽም:: [5]ከእናንተ ማንም ጥበብ ቢጎድለው፣ ሳይነቅፍ በልግስና ለሁሉም የሚሰጠውን እግዚአብሔርን ይለምን፤ ለእርሱም ይሰጠዋል:: [6]ዳሩ ግን ሳይጠራጠር በእምነት ይለምን፤ ምክንያቱም የሚጠራጠር ሰው በነፋስ እንደሚገፋና እንደሚናወጥ የባሕር ማዕበል ነው:: [7]ያ ሰው፣ ከጌታ አንዳች ነገር አገኛለሁ ብሎ አያስብ፤ [8]እርሱ በሁለት ሐሳብ የተያዘና በመንገዱ ሁሉ የማይወላወል ነው::

[9]ዝቅ ያለው ወንድም ከፍ በማለቱ ይመካ:: [10]ባለ ጸጋውም በመውረዱ ይመካ፤ እንደ ሣር አበባ ይረግፋልና:: [11]ፀሓይ በነዲድ ሙቀቷ ወጥታ ሣሩን ታጠወልጋለችና፤ አበባው ይረግፋል፤ ውበቱም ይጠፋል፤ እንዲሁም ባለ ጸጋ ሰው፣ በዕለት ተግባሩ ሲዋትት ሳለ ይጠፋል::

[12]በፈተና የሚጸና ሰው የተባረከ ነው፤ ምክንያቱም ፈተናን ሲቋቋም እግዚአብሔር ለሚወዱት የሰጠውን ተስፋ፣ የሕይወትን አክሊል ያገኛል::

[13]ማንም ሲፈተን፣ 'እግዚአብሔር ፈተነኝ' አይበል፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር በክፉ አይፈተንም፤ እርሱም ማንንም አይፈትንም፤ [14]ነገር ግን እያንዳንዱ የሚፈተነው በራሱ ክፉ ምኞት ሲሳብና ሲታለል ነው:: [15]ምኞትም ከፀነሰች በኋላ ኀጢአትን ትወልዳለች፤ ኀጢአትም ካደገች በኋላ ሞትን ትወልዳለች::

[16]የተወደዳችሁ ወንድሞቼ ሆይ፤ አትታለሉ:: [17]በጎ ስጦታና ፍጹም በረከት ሁሉ ከላይ ከሰማይ ብርሃናት አባት ይወርዳሉ፤ በእርሱ ዘንድ መለዋወጥ ከመዞር የተነሣ የሚያርፍ ጥላም የለም:: [18]የፍጥረቱ በኵራት እንድንሆን በገዛ ፈቃዱ በእውነት ቃል ወለደን::

## ሰምቶ በሥራ ላይ ማዋል

[19]የተወደዳችሁ ወንድሞቼ ሆይ፤ ይህን አስተውሉ፤ ሰው ሁሉ ለመስማት የፈጠነ፣ ለመናገር የዘገየ፣ ለቍጣም የዘገየ ይሁን፤ [20]የሰው ቍጣ የእግዚአብሔርን ጽድቅ አያመጣምና:: [21]ስለዚህ ርኵሰትንና ተንሰራፍቶ የሚገኘውን ክፋትን አስወግዳችሁ ነፍሳችሁን ማዳን የሚችለውን፣ በውስጣችሁም የተተከለውን ቃል በትሕትና ተቀበሉ::

[22]ቃሉ የሚናገረውን አድርጉ እንጂ ሰሚዎች ብቻ ሆናችሁ ራሳችሁን አታታልሉ:: [23]ቃሉን የሚሰማ፣ ነገር ግን የሚለውን የማይፈጽም ሰው ፊቱን በመስተዋት እንደሚያይ ሰው ነው፤ [24]ራሱንም አይቶ ይሄዳል፤ ወዲያውም ምን እንደሚመስል ይረሳል፤ [25]ነገር ግን ነጻ የሚያወጣውን ፍጹም ሕግ ተመል

1፥1 ዘጸ32፥26፤ የሐ7፥35፤ ሐሥ15፥13፡ 23፡26፥7፡ሮሜ1፥1፤ ቲቶ1፥1፡1ጴጥ1፥1
1፥2 ቍ12፤ ማቴ5፥12፤ ዕብ10፥34፡12፥11
1፥3 ዕብ10፥36፤ 1ጴጥ1፥7
1፥4 1ቆሮ2፥6
1፥5 1ነገ3፥9፡10፤ መዝ51፥6፤ምሳ2፥3-6፤ ዳን1፥17፡2፥21፤ ማቴ7፥7
1፥6 ማቴ21፥21፤ ማር11፥24
1፥8 መዝ119፥113፤ ያዕ4፥8፡2ጴጥ2፥14
1፥9 ማቴ23፥12
1፥10 ኢዮ14፥2፤ መዝ103፥15፡16፤ ኢሳ40፥6፡7፤ 1ቆሮ7፥31፡1ጴጥ1፥24
1፥11 ዝ102፥4፡11፤ ኢሳ40፥6፡8፤ማቴ20፥12
1፥12 ቍ2፤ዘፍ22፥1፤ ዘፀ20፥6፡1ቆሮ2፥9፤ 8፥3፡9፥25፤ያዕ2፥5፤ 5፥11፡1ጴጥ3፥14
1፥14 ምሳ19፥3
1፥15 ዘፍ3፥6፤ ኢዮ15፥35፤መዝ7፥14፤ ኢሳ59፥4፡ሮሜ6፥23
1፥16 ቍ19፤ 1ቆሮ6፥9፤ያዕ2፥5
1፥17 ዘፍ1፥16፤ ዘኍ23፥19፤መዝ85፥12፤ 102፥27፡136፥7፤ ዳን2፥22፤ሚል3፥6፤ የሐ3፥27፤ያዕ3፥15፡ 17፡1ዮሐ1፥5
1፥18 ኤር2፥3፤ የሐ1፥13፡2ጢሞ2፥15፤ ራእ14፥4
1፥19 ቍ16፤ ምሳ10፥19፤ያዕ2፥5፤ 3፥3-12 1፥20 ማቴ5፥22
1፥21 ኤፌ1፥13፡4፥22፡1፥22 ማቴ7፥21፤ ያዕ2፥14-20 1፥25 መዝ19፥7፤ የሐ8፥32፡13፥17፤ ገላ2፥4፤ያዕ2፥12

1፥1 *ያዕቆብ*፤ በዚህ መጽሐፍ "መግቢያ" ላይ፣ "ጸሐፊው" የሚለውን ርእስ ይመልከቱ:: *አገልጋይ*፤ የሮሜ 1፥1 ማብ ይመ:: *ዐሥራ ሁለቱ ወገኖች*፤ በመግቢያው ላይ፣ ተደራሲ የሚለውን ርእስ ይመ::

1፥2 *ወንድሞቼ*፤ ያዕቆብ በዚህ አጭር መልእክቱ ውስጥ ተደራስያኑን 15 ጊዜ፣ "ወንድሞች" ይላቸዋል:: መልእክቱ ብዙ ተግሣፅ ያዘለ ቢሆንም እንኳ፣ የሚገሥጻቸው በወንድማማች ፍቅር ነው:: *መከራ*፤ እዚህ ላይ፣ "መከራ" የሚለውና በቍ 13 ላይ፣ ሲፈተን የሚለው ቃል በግሪኩ ሥርወ ቃላቸው አንድ ነው፤ ከቍ 2-3 ላይ ባለው ክፍል፣ መከራ የሚለው ቃል ጥቅም ላይ የዋለው፣ በክርስቲያኖች ላይ ከውጪ የሚነሣውን መከራ ለማመልከት ሲሆን፣ ከቍ 13-15 ላይ ባለው ክፍል ደግሞ ኀጢአትን ለማድረግ ከውስጥ የሚመነጭን ፍላጎት ለማሳየት ጥቅም ላይ ውሎ ይገኛል::

1፥5 *ጥበብ*፤ አንድ ሰው መከራን፣ "እንደ ሙሉ ደስታ" እንዲቈጥረው (ቍ 2) የሚያስችል ማለት ነው:: ጥበብ ዕውቀትን በመገብየት የሚገኝ ብቻ ሳይሆን፣ መንፈሳዊ ትምህርትን ከሕይወት ጋር ማዛመድ ነው (ምሳ 1፥2-4፤ 2፥10-15፤ 4፥5-9፤ 9፥10-12 ይመ)::

1፥6 *የባሕር ማዕበል*፤ ኤፌ 4፥14 ይመ::

1፥9-10 *ዝቅ ያለው ወንድም ... ባለጸጋውም*፤ ያዕቆብ ስለ ጥበብ (ቍ 5-8)፣ ስለ ድኻና ስለ ባለ ጸጋ ሰው (ቍ 9-11) የጻፈው ስለ መከራ በጻፈበት ክፍል መካከል (ቍ 2-4 እና ቍ 12) ስለሆነ፣ ከቍ 5-11 ያለው ክፍል ከመከራ ጋር የሚገናኝ ሊሆን ይችላል:: በድኽነት የሚሠቃይ ክርስቲያን አሁን በክርስቶስ ባገኘው መንፈሳዊ በረከትና (2፥5 ይመ) ጌታ ደግሞ ሲመጣ በሚያገኘው በረከት (ቍ 9) ይመካ፤ ሀብታም ክርስ ቲያንም ዝቅ ሊያደርገው በሚችል መከራ እንኳ ይመካ (ቍ 10)::

1፥12 *የተባረከ*፤ ኤር 17፥7-8፤ ማቴ 5፥3-12 ይመ፤ እንዲሁም የመዝ 1፥1፤ ማቴ 5፥3፤ ራእ 1፥3 ማብ ይመ:: *ሕይወት*፤ "ያገኛል" የሚለው የዐረፍተ ነገሩ ማሰሪያ አንቀጽ የወደፊት ጊዜ ስለሆነ፣ የሚመለከተው ዘላለማዊ ሕይወትን ነው:: *አክሊል*፤ ይህ ቃል በግሪኩ፣ ተወዳድሮ ባሸነፈ ሯጭ ወይም ድል ተጐናጽፎ ከጦር ሜዳ በተመለሰ መሪ ራስ ላይ የሚደፋን አበባ ጕንጕን የሚያመለክት ነው (2ጢሞ 4፥8፤ 1ጴጥ 5፥4 ይመ፤ ራእ 2፥10 እና ማብራሪያውን ይመ)::

1፥13 *ሲፈተን*፤ በቍ 11-13 ላይ ግሡ አንድ ሰው ኀጢአትን ለመቋቋም ያለው ግበረ ገባዊ ጥንካሬ ምን ያህል እንደሆነ ለማወቅ የሚደረገውን ፈተና የሚያመለክት ነው (የማቴ 4፥1 ማብ ይመ):: *እግዚአብሔር ክፉ ለማድረግ አይፈተንም*፤ እግዚአብሔር ቅዱስ ስለሆነ በኀጢአት አይሳብም:: ወይም *እርሱ ማንንም አይፈትንም*፤ የዘፍ 22፥1 ማብ ይመ::

*1፥15*፤ ሔዋን (ዘፍ 3፥6-22) እንዲሁም ዳዊት (2ሳሙ 11፥2-17) በተፈተኑ ጊዜ ደረጃ በደረጃ የተፈጸሙት ሦስት ነገሮች ምኞት፣ ኀጢአትና ሞት ናቸው::

1፥17 *በጎ ስጦታና ፍጹም በረከት ሁሉ ከሰማይ ብርሃናት አባት ከላይ ይወርዳሉ* ቍ 5፥3–17 ይመ:: *ብርሃናት አባት*፤ እግዚአብሔር ለምድር ብርሃን የሚሰጡትን የሰማይ አካላት የፈጠራቸው እርሱ ስለሆነ፣ እነዚህ ነገሮች ቢለ ወጡ እንኳ እርሱ ጸንቶ ይኖራል::

1፥18 *ወለደን*፤ በሥጋ ሳይሆን እንደ ገና በመንፈስ መወለድን ያሳያል (ዮሐ 3፥3-8 ይመ):: *በእውነት ቃል*፤ የምሥራቹን ቃል ማለት ነው (1ጴጥ 1፥23-25 ይመ):: *በኵራት*፤ ዘሌ 23፥9-14 ይመ:: በመከር ወቅት መጀመሪያ ላይ የሚገኘው የእህል ነዶ፣ ምርት እንዳለና የሚሰበሰብበትም ጊዜ ሩቅ እንዳልሆነ የሚያመለክት ዐይነተኛ ምልክት እንደሆነ ሁሉ፣ ቀደምት ክርስቲያኖችም ከእነርሱ በኋላ እጅግ ብዙ ሕዝብ ዳግም ልደት እንደሚያገኝ የሚያመለክቱ ናቸው::

1፥19 *ሰው ሁሉ...ለመናገር የዘገየ ይሁን*፤ ቍጥር 26 ይመ::

1፥21 *ቃል*፤ የእግዚአብሔርን ቃል ማለት ነው::

1፥25 *ፍጹም ሕግ*፤ የክርስትና ግበረ ገባዊና ሥነ ምግባራዊ ትምህርት መሠረት ያደረገው ዐሥርቱ ትእዛዛትን

ክቶ የሚጸና፣ የሰማውን የሚያደርግና የማይረሳ ሰው በሥራው የተባረከ ይሆናል።

[26]አንደበቱን ሳይገታ፣ ልቡን እያሳተ ሃይማኖተኛ ነኝ የሚል ሰው፣ ራሱን ያታልላል፤ ሃይማኖቱም ከንቱ ነው። [27]በእግዚአብሔር አብ ፊት ንጹሕና ነውር የሌለበት ሃይማኖት ይህ ነው፤ ወላጆቻቸው የሞቱባቸውን ልጆችና ባሎቻቸው የሞቱባቸውን ሴቶች በችግራቸው መርዳትና ከዓለም ርኵሰት ራስን መጠበቅ ነው።

## አድልዎ ማድረግ አይገባም

**2** ወንድሞቼ ሆይ፤ ክቡር በሆነው በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ የምታምኑ እንደመሆናችሁ አድልዎ አታድርጉ። [2]የወርቅ ቀለበት ያደረገና ያማረ ልብስ የለበሰ ሰው ወደ ጉባኤያችሁ ቢመጣ እንዲሁም ያደፈ ልብስ የለበሰ ድኻ ሰው ቢገባ፣ [3]ያማረ ልብስ ለለበሰው የተለየ አክብሮት በማሳየት፣ “ለአንተ የሚሆን መልካም መቀመጫ ይኸውልህ” ብትሉትና ድኻውን ሰው ግን፣ “አንተ በዚያ ቁም” ወይም “ከእግሬ በታች በወለሉ ላይ ተቀመጥ” ብትሉት፣ [4]በመካከላችሁ አድልዎ ማድረጋችሁ አይደለምን? ደግሞስ በክፉ ሐሳብ የተያዛችሁ ፈራጆች መሆናችሁ አይደለምን?

[5]የተወደዳችሁ ወንድሞቼ ሆይ፤ ስሙ፤ እግዚአብሔር በእምነት ባለጸጋ እንዲሆኑና እርሱን ለሚወዱም ተስፋ የተሰጣቸውን መንግሥት እንዲወርሱ የዚህን ዓለም ድኾች አልመረጠምን? [6]እናንተ ግን ድኾችን አዋረዳችሁ፤ እናንተን የሚያስጨንቋችሁ ሀብታሞች አይደሉምን? ወደ ፍርድ ቤት የሚጐትቷችሁስ እነርሱ አይደሉምን? [7]በእናንተ የተጠራውን ክቡር የሆነውን ስም የሚሳደቡ እነርሱ አይደሉምን?

[8]በመጽሐፍ፣ “ባልንጀራህን እንደ ራስህ አድርገህ ውደድ” ተብሎ የተጻፈውን ክቡር ሕግ ብትፈጽሙ መልካም እያደረጋችሁ ነው። [9]አድልዎ ብታደርጉ ግን ኀጢአት መሥራታችሁ ነው፤ በሕግም ፊት እንደ ሕግ ተላላፊዎች ትቈጠራላችሁ፤ [10]ምክንያቱም ሕግን ሁሉ የሚፈጽም ነገር ግን በአንዱ የሚሰናከል ቢኖር፣ ሁሉን እንደ ተላለፈ ይቈጠራል። [11]“አታመንዝር” ያለ እርሱ ራሱ “አትግደልም” ብሎአልና። ባታመንዝር፣ ነገር ግን ብትገድል፣ ሕግ ተላላፊ ሆንሃል።

[12]ስትናገሩም ሆነ ስታደርጉ ነጻነት በሚሰጠው ሕግ እንደሚፈረድባቸው ሰዎች ሁኑ፤ [13]ምክንያቱም ምሕረት ያላደረገ ሁሉ ያለ ምሕረት ይፈረድበታል፤ ምሕረት በፍርድ ላይ ያይላል።

## እምነትና ሥራ

[14]ወንድሞቼ ሆይ፤ አንድ ሰው እምነት አለኝ ቢል ሥራ ግን ባይኖረው ምን ይጠቅመዋል? እንዲህ ያለው እምነት ሊያድነው ይችላልን? [15]አንድ ወንድም ወይም አንዲት እኅት የሚለብሱት ልብስም ሆነ የሚመገቡት ምግብ አጥተው፣ [16]ከእናንተ መካከል አንዱ፣ “በሰላም ሂዱ፤ አይብረዳችሁ፤ ጥገቡ” ቢላቸው፣ ለሰውነታቸው ግን የሚያስፈልጋቸውን ባይሰጣቸው፣ ምን ይጠቅማቸዋል? [17]እንዲሁ ሥራ የሌለው እምነት በራሱ የሞተ ነው።

1፥26 መዝ34፥13፤ 39፥1፤141፥3፤ያዕ3፥2-12፤ 1ጴጥ3፥10
1፥27 ዘዳ14፥29፤ ኢዮ31፥16:17:21፤ መዝ146፥9፤ ኢሳ1፥17:23፤ ማቴ25፥36፤ሮሜ12፥2፤ ያዕ4፥4፤2ጴጥ1፥4፤2፥20
2፥1 ቍ9፤ ዘሌ19፥15፤ዘዳ1፥17፤ ምሳ24፥23፤ሐሥ7፥2፤ 10፥34፤1ቆሮ2፥8
2፥4 ዮሐ7፥24
2፥5 ኢዮ34፥19፤ ማቴ25፥34፤ሉቃ12፥21፤ 1ቆሮ1፥26-28፤ ያዕ1፥12:16:19፤ ራእ2፥9
2፥6 ሐሥ8፥3፤ 16፥19፤1ቆሮ11፥22
2፥8 ዘሌ19፥18፤ ማቴ5፥43
2፥9 ቍ1፤ዘዳ1፥17
2፥10 ማቴ5፥19፤ ገላ3፥10፤5፥3፤ያዕ3፥2
2፥11 ዘፀ20፥13: 14፤ዘዳ5፥17:18
2፥12 ማቴ16፥27፤ ያዕ1፥25
2፥13 ማቴ5፥7፤ 9፥13፤12፥7፤18፥32-35፤ ሉቃ6፥37
2፥14 ማቴ7፥26፤ ያዕ1፥22-25
2፥15 ማቴ25፥35:36
2፥16 ሉቃ3፥11፤ 1ዮሐ3፥17:18
2፥17 ቍ20:26፤ገላ5፥6

ያካተተውን የብሉይ ኪዳን ግብረገባዊ ሕግ ነው (መዝ 19፥7 ይመ)፤ ነገር ግን ፍጹምነት ያገኘው በኢየሱስ ክርስቶስ ነው። ነጻ የሚያወጣውን፤ ክርስቲያን የኀጢአት ባሪያ ከሆነው ሰው ጋር ሲነጻጸር (ዮሐ 8፥34)፣ ግብረገባዊ ሕግጋትን በመታዘዙ እግዚአብሔር ባዘጋጀለት ነጻነት ውስጥ በደስታ ይኖራል (2፥12 ተመልከት)።

1፥26 *ሃይማኖተኛ*፤ የሃይማኖት ውጫዊ መገለጫ የሆኑትን የሚያመለክት ነው፤ እነዚህም ለችግረኛ መመጽወት፣ ጾምና ምሕላ እንዲሁም ሥርዐተ አምልኮ ናቸው።

*1፥27*፤ ኤር 22፥16 ይመ። *ዓለም*፤ ግዑዙን ዓለም ሳይሆን፣ ሰዎች ለእግዚአብሔር ባለመታዘዝ በሚፈጽሙት ዐመፅና ከእርሱም በመለየታቸው ምክንያት በውስጣቸው የነገሠውን ዓለም ነው (1ዮሐ 2፥15 ይመ)።

2፥1 *የምታምኑ እንደሆናችሁ አድልዎ አታድርጉ*፤ በእግዚአብሔር ዘንድ አድልዎ የለም፤ አማኞችም አድልዎ ሊያደርጉ አይገባም።

2፥2 *ጉባኤያችሁ*፤ ስብሰባችሁ፤ ቃሉ በግሪኩ ምኵራብ የሚል ትርጕም አለው።

*2፥5-13*፤ ያዕቆብ ለባለጠጎች ማድላት የማይገባ መሆኑን ለማስረዳት ሦስት የመቃወሚያ ሐሳቦችን ያቀርባል:- (1) ባለጠጎች ድኾችን ማለትም ክርስቲያኖችን ያሳድዳሉ (ቍ 5-7)፤ (2) አድልዎ የፍቅርን ክቡር ሕግ የሚቃረን በመሆኑ ኀጢአት ነው (ቍ 8-11)፤ (3) አድልዎ ፍርድን ያስከትላል (ቍ 12-13)።

2፥5 *እግዚአብሔር ... የዚህን ዓለም ድኾች አልመረጠምን?* ሉቃ 6፥20፤ 1ቆሮ 1፥26-31 ይመ። *መንግሥት*፤ አዲስ ልደት ያገኙ (ዮሐ 3፥3:5) በሙላት የሚገቡበት መንግሥት ነው (ማቴ 25፥34:46)።

2፥8 *ክቡር ሕግ*፤ የፍቅር ሕግ (ዘሌ 19፥18) “ክቡር ሕግ” ይባላል፤ ምክንያቱም በሰዎች መካከል ያለው ግንኙነት የሚዳኝባቸው ሕጎች ሁሉ፣ ሥረ መሠረታቸው ይህ ታላቅ ሕግ ስለ ሆነ ነው። እንዲህ ላሉት የግንኙነት ሕጎች ሁሉ መነሻቸውም መድረሻቸውም ይህ ሕግ ነው (ማቴ 22፥36-40፤ ሮሜ 13፥8-10)።

2፥10 *ሁሉን እንደ ተላለፈ ይቈጠራል*፤ ሕጉ የእግዚአብሔር ባሕርይና ፈቃድ መግለጫ ነው፤ ስለዚህ ከሕጉ አንዲቱን ትእዛዝ መተላለፍ፣ ከእግዚአብሔር ፈቃድ መውጣትና ሕጉን ሙሉ በሙሉ መጣስ ማለት ነው (ከማቴ 5፥18-19፤ 23፥23 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥12 *እንደሚፈረድባቸው*፤ የያዕቆብን ተደራስያን ቀድሞውኑ የመጨረሻ ዕጣ ፈንታቸውን (ዮሐ 5፥24) የሚያውቁ አማኞች ስለ ሆኑ (ቍ1)፣ ክፍሉ የሰውን ዕድል ፈንታ ስለሚወስነው የመጨረሻው ፍርድ የሚናገር አይደለም፤ ነገር ግን ይህ ፍርድ መጨረሻውን ለክርስቲያኖች ስለሚሰጠው ሽልማት ነው (1ቆሮ 3፥12-15፤ 2ቆሮ 5፥10፤ ራእ 22፥12)።

2፥13 *ምሕረት በፍርድ ላይ ያይላል*፤ አንድ ሰው መሓሪ ከሆነ፣ እግዚአብሔርም በፍርድ ቀን ምሕረት ያደርግለታል (ምሳ 21፥13፤ ማቴ 5፥7፤6፥14-15፤ 18፥21-35 ይመ)።

*2፥14-26*፤ በቍ 14-20:24:26 ላይ፣ “እምነት” የሚለው ቃል ድነት ስለሚያስገኘው እውነተኛ እምነት የተጻፈ አይደለም፤ ነገር ግን አጋንንት እንደሚያምኑት ዐይነት (ቍ19)፣ ከንቱና (ቍ 20) ሙት የሆነውን (ቍ 26) እምነት ለማመልከት የገባ ቃል ነው። ይህ እምነት የክርስቶስን አዳኝነት ማመን ሳይሆን፣ በአእምሮ ዕውቀት ላይ የተመሠረተ ነው። ያዕቆብ ሰው በእውነተኛ እምነት ሳይሆን በሥራ ይድናል አላለም፤ ይልቁንም ሰው የሚጸድቀው በእምነት ብቻ ነው፤ የሚያድን እምነት ደግሞ ብቻውን ሳይሆን፣ ሥራን ገንዘቡ ያደረገ ነው። እውነተኛ እምነት በጎ ሥራ ይከተለዋል፤ ድነት የሚገኘው ግን ክርስቶስን በማመን ነው (ስለ መጽደቅ የበለጠ ለመረዳት የሮሜ 3፥24 ማብ ይመ)።

*2፥15-16*፤ ይህ እውነተኛ ስላልሆነ እምነት የቀረበው ገለጻ፣ በ1ዮሐ3፥17 ላይ እውነተኛ ስላልሆነ ፍቅር ከቀረበው ገለጻ ጋር ተጓዳኝ ነው፤ የመጀመሪያው ክፍል እውነተኛ እምነት በሥራ እንደሚገለጽ የሚያስተምር ሲሆን፣ ሁለተኛ ክፍል ደግሞ እውነተኛ ፍቅር ሥራን ገንዘቡ እንዳደረገ የሚገልጽ ነው።

18ነገር ግን አንድ ሰው “አንተ እምነት አለህ፤ እኔ ሥራ አለኝ” ይላል። እምነትህን ከሥራ ለይተህ አሳየኝ፤ እኔም እምነቴን በሥራዬ አሳይሃለሁ። 19አንድ እግዚአብሔር እንዳለ ታምናለህ፤ መልካም ነው፤ አጋንንትም ይህን ያምናሉ፤ በፍርሀትም ይንቀጠቀጣሉ።

20አንተ ከንቱ ሰው! እምነት ያለ ሥራ ዋጋ የሌለው[ሀ] መሆኑን ለማወቅ ማስረጃ ትፈልጋለህን? 21አባታችን አብርሃም ልጁን ይስሐቅን በመሠዊያው ላይ ባቀረበ ጊዜ በሥራ የጸደቀ አልነበረምን? 22በዚህም እምነት ከሥራው ጋር አብሮ ይሠራ እንደነበር ታያለህ፤ እምነትም በሥራ ፍጹም ሆነ። 23“አብርሃም በእግዚአብሔር አመነ፤ ጽድቅም ሆኖ ተቈጠረለት” የሚለው የመጽሐፍ ቃል ተፈጸመ፤ እርሱም የእግዚአብሔር ወዳጅ ተባለ። 24እንግዲህ በእምነት ብቻ ሳይሆን በሥራ እንዲጸድቅ ታያላችሁ።

25እንዲሁም ጋለሞታዪቱ ረዓብ መልእክተኞቹን ተቀብላ በሌላ መንገድ በሰደደቻቸው ጊዜ በሥራ አልጸደቀችምን? 26ከመንፈስ የተለየ ሥጋ የሞተ እንደ ሆነ ከሥራም የተለየ እምነት የሞተ ነው።

## አንደበትን መግታት

**3** ወንድሞቼ ሆይ፤ ከእናንተ ብዙዎች አስተማሪዎች አይሁኑ፤ ምክንያቱም እኛ አስተማሪዎች የሆንን የባሰ ፍርድ እንደ ምንቀበል ታውቃላችሁ። 2ሁላችንም በብዙ ነገር እንሰናከላለን፤ በንግግሩ የማይሰናከል ማንም ሰው ቢኖር እርሱ ሰውነቱን ሁሉ መቈጣጠር የሚችል ፍጹም ሰው ነው።

3ፈረሶች እንዲታዘዙልን ልጓም በአፋቸው ውስጥ ስናስገባ፣ መላ ሰውነታቸውን መምራት እንችላለን። 4ወይም መርከቦችን ተመልከቱ፤ ምንም እንኳ እጅግ ትልቅና በኀይለኛ ነፋስ የሚነዱ ቢሆኑም የመርከቡ ነጂ በትንሽ መሪ ወደሚፈልገው አቅጣጫ ይመራቸዋል። 5እንዲሁም ምላስ ትንሽ የሰውነት ክፍል ሆና ሳለ በታላላቅ ነገሮች ትኵራራለች፤ ትልቅ ጫካ በትንሽ እሳት እንዴት ተቃጥሎ እንደሚጠፋ አስተውሉ፤ 6ምላስም እንደ እሳት ናት፤ በሰውነት ክፍሎቻችን መካከል የምትገኝ የክፋት
ዓለም ናት፤ ሰውነትን ሁሉ ታረክሳለች፤ ደግሞም የፍጥረትን ሩጫ ታቃጥላለች፤ ራሷም በገሃነም ትቃጠላለች።

7ማናቸውም ዐይነት እንስሳ፣ አዕዋፍ እንዲሁም በምድር ላይ የሚሳቡና፥ በባሕር ውስጥ የሚኖሩ ፍጥረታት ሁሉ መገራት ችለዋል፤ በሰውም ተገርተዋል። 8ነገር ግን ምላስን መግራት የሚችል ማንም ሰው የለም፤ የሚገድል መርዝ የሞላባትና ዕረፍት የሌላት ክፉ ነገር ናት።

9በምላሳችን ጌታንና አብን እንባርካለን፤ በእርስዋም በእግዚአብሔር አምሳል የተፈጠሩትን ሰዎች እንረግማለን። 10ከአንድ አፍ በረከትና መርገም ይወጣሉ፤ ወንድሞቼ ሆይ፤ ይህ ሊሆን አይገባም። 11ከአንድ ምንጭ ጣፋጭ ውሃና መራራ[ለ] ውሃ ይመነጫልን? 12ወንድሞቼ ሆይ፤ በለስ ወይራን ወይንም በለስን ሊያፈራ ይችላልን? እንዲሁም ከጨው ውሃ ጣፋጭ ውሃ ሊገኝ አይችልም።

## ሁለት ዐይነት ጥበብ

13ከእናንተ መካከል ጥበበኛና አስተዋይ የሆነ ሰው ማን ነው? ሥራውን ከጥበብ በሆነ በመልካም አኗኗር ያሳይ። 14ነገር ግን መራራ ቅንአትና ራስ ወዳድነት በልባችሁ ቢኖር ኵራት አይሰማችሁ፤ እውነትንም አትካዱ። 15እንዲህ ያለችዋ ጥበብ ከላይ አይደለችም፤ ነገር ግን ከምድር ከሥጋና ከአጋንንት ናት። 16ቅናትና ራስ ወዳድነት ባሉበት ስፍራ በዚያ ሁከትና ክፉ ሥራ ሁሉ ይገኛሉ።

[ሀ]20 አንዳንድ ጥንታዊ ያለሆኑ ቅጆች፣ ሙት ይሉታል
[ለ]11 በግሪኩ፣ ጨው ይለዋል

2፥18 ማቴ7፥16:17፤ ሮሜ3፥28፤ዕብ11፤ ያዕ3፥13
2፥19 ዘዳ6፥4፤ ማቴ8፥29፤ማር12፥29፤ ሉቃ4፥34፤1ቆሮ8፥4-6
2፥20 ቍ17:26
2፥21 ዘፍ22፥9:12
2፥22 ዕብ11፥17፤ 1ተሰ1፥3
2፥23 ዘፍ15፥6፤ 2ዜና20፥7፤ ኢሳ4፥8፤ሮሜ4፥3
2፥25 ዕብ11፥31
2፥26 ቍ17:20
3፥1 ማቴ7፥1፤ሮሜ 2፥21፤ኤፌ4፥11
3፥2 1ነገ8፥46፤ መዝ39፥1፤ምሳ10፥19፤ ማቴ12፥37፤ ሮሜ3፥9-20 ያዕ1፥26፤2፥10፤ 1ጴጥ3፥10፤1ዮሐ1፥8
3፥3 መዝ32፥9
3፥5 መዝ12፥3:41 73፥8:9
3፥6 ምሳ16፥27፤ ማቴ5፥22፤15፥11:18: 19
3፥8 መዝ140፥3፤ ሮሜ3፥13
3፥9 ዘፍ1፥26:27፤ 1ቆሮ11፥7
3፥12 ማቴ7፥16
3፥13 ያዕ2፥18፤ 1ጴጥ2፥12
3፥14 ቍ16፤ 2ቆሮ12፥20፤ያዕ5፥19
3፥15 ቍ17፤ 1ጢሞ4፥1፤ያዕ1፥17
3፥16 ቍ14፤ ገላ5፥20:21

2፥18 *አንተ እምነት አለህ፤ እኔ ሥራ አለኝ፤* ስሕተቱ፣ “የእምነት” ክርስቲያን እና፣ የሥራ ክርስቲያን በማለት እምነትንና ሥራን ለየብቻ በተናጠል ማቅረቡ ነው። *እምነትህን ከሥራ ለይተህ አሳየኝ፤* ያዕቆብ ይህ ምፀት እንጂ በፍጹም ሊሆን የማይችል ነገር እንደ ሆነ ይገልጻል።

2፥19 *አንድ እግዚአብሔር፤* በአይሁድ ትምህርተ ሃይማኖት በጣም የታወቀውና በዕብራይስጡ፣ “ሽማ” (ስማ) የሚል አምላክ አንድ ብቻ መሆኑን የሚገልጽ የእምነት አንቀጽ ነው (ዘዳ 6፥4፤ ማር 12፥29)።

*2፥21፤* ክፍሉን ከዐውዱ ነጥለን ከተመለከትነው፣ ሰው ድነት የሚያገኘው በእምነት እንጂ በሥራ አይደለም ከሚለው የመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት ጋር የሚቃረን ይመስላል (ሮሜ 3፥28፤ ገላ 2፥15-16)። ያዕቆብ የሚለው ግን፣ የጽድቅ ሥራ የእውነተኛ እምነት መገለጫ እንጂ ለድነት የሚያበቃ አይደለም፤ ለዚህ ማስረጃ አድርጎ የሚያቀርበው፤ “አብርሃም በእግዚአብሔር አመነ ጽድቅም ሆኖ ተቈጠረለት” (ቍ 23) የሚለውን ነው፤ ከዚህ ክፍል የምንማረው፣ ጽድቅ ሆኖ የተቈጠረለት እምነቱ እንጂ ሥራው አይደለም። (በዘፍ 15፥6) የሚለው። የሚያድን እምነት በጎ ሥራን ገንዘቡ ያደረገ ነው።

2፥23 *የእግዚአብሔር ወዳጅ፤* ይህ አብርሃም ከእግዚአብሔር ጋር የነበረውን ወዳጅነትና (2ዜና20፥7 ይመ) እግዚአብሔር ምን ያህል እንደ ተቀበለው የሚያስገነዝበን ነው።

2፥24 *በእምነት ብቻ ሳይሆን፤* (የ2፥14-26 ማስታወሻ ይመ)።

2፥25 *ጋለሞታዪቱ ረዓብ፤* በዚህ ስፍራ የረዓብ ስም በመልካም የተወሳው፣ ያዕቆብ የግልሙትናን ሕይወት እንደ በጎ ነገር ስለቈጠረው ሳይሆን፣ ሰላዮቹን በመረዳቷ (ኢሱ 2) የታየውን እምነት በማድነቅ ብቻ ነው (ዕብ 11፥31 ይመ)።

3፥1 *የባሰ ፍርድ እንደምንቀበል፤* አስተማሪ ከሌላው ይልቅ ተጽዕኖ ማድረግ ስለሚችል፣ ያለበት ኀላፊነት የዚያኑ ያህል ከባድ ነው (ሉቃ 20፥47 ይመ፤ ከማቴ 23፥1-33 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥2 *ፍጹም ሰው፤* ምላስን መቈጣጠር አስቸጋሪ ስለሆነ፣ ምላሱን መቈጣጠር የሚችል፣ በማንኛውም ረገድ ሕይወቱን መቈጣጠር ይችላል።

3፥6 *የክፋት ዓለም፤* ዓለም በውድቀት ገጽታዋ እንደ ምትመስለው ማለት ነው። *ራስዋም በገሃነም ትቃጠላለች፤* ይህ ከምላስ ለሚወጣው የክፋት መርዝ ምንጩ ዲያብሎስ መሆኑን የሚያመለክት ሥዕላዊ ገለጻ ነው (ዮሐ 8፥44 ይመ)። የማቴ 5፥22፤ ሉቃ 16፥23 ማብ ይመ።

3፥9 *በእግዚአብሔር አምሳል፤* ሰው በእግዚአብሔር አምሳል የተፈጠረ ስለ ሆነ (ዘፍ 1፥26-27)፣ ሰውን መርገም እግዚአብሔርን እንደ መርገም ይቈጠራል (ዘፍ 9፥6 ይመ)፤ እንዲሁም የዘፍ 1፥26 ማብ ይመ።

3፥13 *ጥበበኛ፤* የ1፥5 ማብ ይመ።

3፥15 *ከላይ፤* ከእግዚአብሔር ማለት ነው (1፥5:17፤ 1ቆሮ 2፥6-16 ይመ)።

3፥16 *ሁከትና፤* “እግዚአብሔር የሰላም አምላክ እንጂ፣ የሁከት አምላክ አይደለም” (1ቆሮ 14፥33)።

[17]ከሰማይ የሆነችው ጥበብ ግን በመጀመሪያ ንጽሕት ናት፤ በኋላም ሰላም ወዳድ፣ ታጋሽ፣ እሺ ባይ፣ ምሕረትና መልካም ፍሬ የሞላባት፣ አድልዎና ግብዝነት የሌለባት ናት። [18]የጽድቅም ፍሬ ሰላምን ለሚያደርጉ በሰላም ይዘራል።

## ራሳችሁን ለእግዚአብሔር አስገዙ

**4** በእናንተ መካከል ያለው ጦርነትና ጠብ ከየት የመጣ ነው? በውስጣችሁ ከሚዋጉት ምኞታችሁ አይደለምን? [2]ትመኛላችሁ፤ ነገር ግን አታገኙም። ትገድላላችሁ፤ በብርቱም ትመኛላችሁ፤ ልታገኙም አትችሉም። ትጣላላችሁ፤ ትዋጋላችሁ፤ አትለምኑምና ለእናንተ አይሆንም።

[3]ትለምናላችሁ ግን አትቀበሉም፤ ለራሳችሁ ሥጋዊ ደስታ በማሰብ በክፉ ምኞት ትለምናላችሁና።

[4]አመንዝሮች ሆይ፤ ከዓለም ጋር ወዳጅ መሆን የእግዚአብሔር ጠላት መሆን እንደ ሆነ አታውቁምን? ስለዚህ የዓለም ወዳጅ መሆን የሚፈልግ ሁሉ የእግዚአብሔር ጠላት ሆኖአል። [5]ወይስ በውስጣችን ያሳደረው መንፈስ አብዝቶ ይቀናል* በማለት መጽሐፍ የተናገረው በከንቱ ይመስላችኋልን? [6]ነገር ግን ጸጋን አብዝቶ ይሰጠናል፤ መጽሐፍም፣

"እግዚአብሔር ትዕቢተኞችን ይቃወማል፤
ለትሑታን ግን ጸጋን ይሰጣል"
ያለው ስለዚህ ነው።

[7]እንግዲህ ራሳችሁን ለእግዚአብሔር አስገዙ፤ ዲያብሎስን ተቃወሙት፤ ከእናንተም ይሸሻል። [8]ወደ እግዚአብሔር ቅረቡ፤ እርሱም ወደ እናንተ ይቀርባል። እናንተ ኀጢአተኞች እጃችሁን አንጹ፤ እናንተ በሁለት ሐሳብ የምትዋልሉ ልባችሁን አጥሩ። [9]ተጨነቁ፤ እዘኑ፤ አልቅሱም። ሳቃችሁ ወደ ኀዘን፣ ደስታችሁም ወደ ትካዜ ይለወጥ። [10]በጌታ ፊት ራሳችሁን አዋርዱ፣ እርሱም ከፍ ከፍ ያደርጋችኋል።

[11]ወንድሞች ሆይ፤ እርስ በርሳችሁ አትወነጃጀሉ፤ ወንድሙን የሚወነጅልና በወንድሙም ላይ የሚፈርድ በሕግ ላይ ክፉ ይናገራል፤ በሕግም ላይ ይፈርዳል። በሕግ ላይ ብትፈርድ ፈራጅ እንጂ ሕግን አድራጊ አይደለህም። [12]ሕግን የሚሰጥና የሚፈርድ አንድ ብቻ ነው፤ እርሱም ሊያድንና ሊያጠፋ የሚችል ነው፤ ነገር ግን በባልንጀራህ ላይ የምትፈርድ አንተ ማን ነህ?

## ስለ ነገ መመካት

[13]እናንተ "ዛሬ ወይም ነገ ወደዚህች ወይም ወደዚያች ከተማ እንሄዳለን፤ በእርሷም አንድ ዓመት እንቈያለን፤ እንነግዳለን፤ እናተርፋለንም" የምትሉ እንግዲህ ስሙ። [14]ነገ የሚሆነውን እንኳ አታውቁም። ሕይወታችሁ ምንድን ናት? ለጥቂት ጊዜ ታይቶ ኋላ እንደሚጠፋ እንፋሎት ናችሁ። [15]ይልቁንም፣ "የጌታ ፈቃድ ቢሆን እንኖራለን፤ ይህን ወይም ያንን እናደርጋለን" ማለት ይገባችኋል። [16]አሁን ግን በትዕቢታችሁ ትመካላችሁ፤ እንዲህ ያለው ትምክህት ሁሉ ክፉ ነው። [17]እንግዲህ መልካም የሆነውን ነገር ማድረግ እንዳለበት እያወቀ የማያደርግ ሰው ኀጢአት ያደርጋል።

## ለጨካኝ ሀብታሞች የተሰጠ ማስጠንቀቂያ

**5** እንግዲህ እናንተ ሀብታሞች ስሙ፤ ስለሚደርስባችሁ መከራ አልቅሱ፤ ዋይ ዋይም በሉ። [2]ሀብታችሁ ሻግቶአል፤ ልብሳችሁንም ብል በልቶታል። [3]ወርቃችሁና ብራችሁ ዝጎአል፤ ዝገቱም በእናንተ ላይ ይመሰክራል፤ ሥጋችሁንም እንደ እሳት ይበላዋል፤ ለመጨረሻው ዘመን ሀብትን አከማችታችኋል። [4]ልብ በሉ፤ እርሻችሁን ሲያጭዱ ለዋሉ ሠራተኞች ያልከፈላችሁት ደመወዝ በእናንተ ላይ ይጮኻል፤ የአጫጆቹም ጩኸት ሁሉን ቻይ

3፥17 ሉቃ6፥36፤ ሮሜ2፥9፤1ቆሮ2፥6፤ ዕብ12፥11፤ያዕ1፥17
3፥18 ምሳ11፥18፤ ኢሳ32፥17፤ ሆሴ10፥12፤ ማቴ5፥9፤ሮሜ14፥19፤ ፊል1፥11
4፥1 ሮሜ7፥23፤ ቲቶ3፥9
4፥2 ማቴ5፥21፡22፤ ያዕ5፥6፤1ዮሐ3፥15
4፥3 መዝ18፥41፤ 66፥18፤ማቴ7፥7፤ 1ዮሐ3፥22፤5፥14
4፥4 ኢሳ54፥5፤ ኤር3፥20፤ሆሴ2፥2-5፤ 3፥1፤9፥1፤ዮሐ15፥19 ሮሜ8፥7፤ያዕ1፥27፤ 1ዮሐ2፥15
4፥5 1ቆሮ6፥19
4፥6 ምሳ3፥34፤ ማቴ23፥12
4፥7 ኤፌ4፥27፤ 6፥11፤1ጴጥ5፥6-9
4፥8 መዝ24፥4፤ 73፥28፤119፥113፤ ኢሳ1፥16፤ ኤር4፥14፤ዘካ1፥3፤ ሚል3፥7፤ዕብ7፥19፤ ያዕ1፥8
4፥9 ሉቃ6፥25
4፥10 ቍ6፤ ኢዮ5፥11፤1ጴጥ5፥6
4፥11 ማቴ7፥1፤ ሮሜ1፥30፤ 2ቆሮ12፥20፤ያዕ1፥22፤ 2፥8፤1ጴጥ2፥1
4፥12 ኢሳ33፥22፤ ማቴ7፥1፤10፥28፤ ያዕ5፥9
4፥13 ምሳ27፥1፤ ሉቃ12፥18-20፤ያዕ5፥1
4፥14 ኢዮ7፥7፤ መዝ39፥5፤102፥3፤ 144፥4፤ኢሳ2፥22
4፥15 ሐሥ18፥21 ዮሐ9፥41
4፥16 1ቆሮ5፥6
4፥17 ሉቃ12፥47፤ ሕዝ30፥2፤ሉቃ6፥24፤ 1ጢሞ6፥9፤ያዕ2፥2-6፤ 4፥13
5፥1 ኢሳ13፥6፤ 5፥2 ኢዮ13፥28፤ መዝ39፥11፤ኢሳ50፥9፤ ማቴ6፥19፡20 5፥3 ቍ7፡8 5፥4 ዘሌ19፥13፤ ዘዳ24፥15፤ ኤር22፥13፤ ሚል3፥5፤ ሮሜ9፥29

*5 ወይም፣ *እግዚአብሔር በውስጣችን እንዲኖር ያሳደረው መንፈስ በቅናት ይመኛል፤ ወይም በውስጣችን እንዲኖረው ያደረገው መንፈስ በቅናት ይመኛል ማለት ነው።*

3፥17 *አድልዎ፤* 2፥1-13 ይመ።

3፥18 *ሰላምን ለሚያደርጉ፤* ከቍ 16 ጋር ያነጻጽሩ። መለያየት ጽድቅን አያመጣም።

4፥2 *ትገድላላችሁ፤* ጥላቻን አግዝፎ ለማሳየት የቀረበ ምሳሌያዊ አነጋገር ነው።

4፥4 *አመንዝሮች፤* በመንፈሳዊ ሕይወታቸው ታማኝነት የጐደላቸው፣ ከእግዚአብሔር ይልቅ ዓለምን የሚወዱ ማለት ነው። መንፈሳዊ አመንዝራነትን በተመለከተ ኤር 31፥32 ይመ። *ዓለም፤* የ1፥27 ማብ ይመ።

4፥5 *መጽሐፍ፤* ያዕቆብ የትኛውን መጽሐፍ ለማለት እንደፈለገ ግልጽ አይደለም *መንፈስ አብዝቶ ይቀናል፤* "በውስጣችን ያሳደረው መንፈስ" ሰውን የፈጠረው እግዚአብሔር መሆኑን ያመለክታል (ዘፍ 2፥7)። የሰው ልጅ በኀጢአት ከመውደቁ የተነሣ፣ መንፈሱ "አብዝቶ ይቀናል"፤ የእግዚአብሔር ጸጋ ግን (ቍ 6) የሰውን ቅናት ማሸነፍ ይችላል። አማራጭ ትርጕሙን ይመ።

*4፥6፤* ምሳ 3፥34 ላይ የተጠቀሰውን በ1 ጴጥ 5፥5 ይመ።

*4፥7-10፤* በግሪኩ እነዚህ ቍጥሮች እያንዳንዳቸው በኀጢአት የተሞላውን የትዕቢት ዝንባሌ ነቅሎ ለመጣል ወዲያውኑ እርምጃ እንዲወሰድ የሚጠይቁ ዐሥር ትእዛዞች ይዘዋል።

4፥7 *ዲያብሎስን ተቃወሙት፤* ኤፌ 6፥11-18፤ 1ጴጥ 5፥8-9 ይመ።

4፥8 *እጃችሁን አንጹ፤* የዘመነ ብሉይ ካህናት የምስክሩ ድንኳን ወዳለበት ወደ እግዚአብሔር ፊት ከመቅረባቸው በፊት እጅና እግራቸውን በናስ መታጠቢያ ውስጥ መታጠብ ነበረባቸው፤ ይህም ካህናት ከኀጢአታቸው እንደነጹ የሚያመለክት ነበር (ዘፀ 30፥17-21)። "ንጹሕ እጅና ቅን ልብ" የሚለውን በመዝ 24፥4 ላይ ይመ።

4፥9 *ተጨነቁ፤ እዘኑ፤ አልቅሱ፤* ንስሓ ግቡ ማለት ነው።

4፥10፤ ማቴ23፥12 ይመ።

4፥11 *ወንድሙን የሚወነጅል...በሕግም ላይ ይፈርዳል፤* የ2፥8 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ዘፀ20፥16፤መዝ15፥3፤50፥19-20፤ ምሳ 6፥16፡19 ይመ። በወንድም ላይ ክፉ መናገር የፍቅርን ሕግ መናቅ ነው።

5፥1 *ሀብታሞች፤* እንደ 2፥2፡6 እነዚህም ሰዎች ክርስቲያኖች አይደሉም፤ ምክንያቱም እያስጠነቀቃቸው ነውና። ከቍ 1-6 ላይ ያለው ክፍል፣ በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት የተለያዩ ክፍሎች ውስጥ በአሕዛብ ላይ ከተነገሩት የፍርድ ዐዋጆች ጋር ተመሳሳይ ናቸው፤ ወይም ደግሞ ለእግዚአብሔር ሕዝብ በቀጥታ የተነገሩ ናቸው (ኢሳ 13-23፤ ኤር 46-51፤ ሕዝ 25-32፤ አሞ 1፥3-2፥16፤ ሶፎ 2፥4-15)።

5፥2 *ልብሳችሁንም፤* በጥንቱ ዓለም ብልጽግና ከሚለካባቸው ነገሮች አንዱ ልብስ ነበር (ሐዋ 20፥33 ይመ)።

5፥3 *ዝገቱ፤* የማከማቸት ውጤት ነው፤ ይህም በስስታም ባለጠጎች ላይ የሚመሰክርባቸውና፤ የሚፈርድባቸው ነው። *ለመጨረሻው ዘመን፤* የሐሥ2፥17፤1ጢሞ 4፥1፤2ጢሞ3፥1፤የዕብ 1፥1፤ የዮሐ 2፥18 ማብ ይመ።

ወደ ሆነው ጌታ ጆሮ ደርሶአል። [5]በምድርም ላይ በምቾትና በመቀማጠል ኖራችኋል፤ ለዕ ርድ‾ ቀን ልባችሁን አወፍራችኋል። [6]እናንተን ያልተቃወሙትን ንጹሐን ሰዎች ኰንናችኋል፤ ገድላችኋልም።

## በመከራ ውስጥ መታገሥ

[7]እንግዲህ ወንድሞች ሆይ፤ ጌታ እስከሚመጣ ድረስ ታገሡ። ገበሬ መሬቱ መልካምን ፍሬ እስከሚሰጥ ድረስ እንዴት እንደሚታገሥ፣ የፊተኛውንና የኋለኛውን ዝናብ እንዴት እንደሚጠባበቅ አስተውሉ። [8]እናንተም እን ዲሁ ታገሡ፤ ልባችሁንም አጽኑ፤ ምክንያቱም የጌታ መምጫ ተቃርቦአል። [9]ወንድሞች ሆይ፤ እርስ በርሳችሁ አታጕረምርሙ፤ ያለ ዚያ ይፈረድባችኋል፤ እነሆ ፈራጁ በበር ላይ ቆሞአል።

[10]ወንድሞች ሆይ፤ በጌታ ስም የተናገሩትን ነቢያት የመከራና የትዕግሥት ምሳሌ አድርጋችሁ ተመልከቱ። [11]በትዕግሥት የጸኑትን የተባረኩ አድርገን እንደምንቈጥር ታውቃ ላችሁ፤ ኢዮብ እንዴት ታግሦ እንደ ጸና ሰምታችኋል፤ ጌታም በመጨረሻ ያደረገ ለትን አይታችኋል። ጌታ እጅግ ርኅሩኅና መሐሪ ነው።

[12]ከሁሉም በላይ ወንድሞቼ ሆይ፤ በሰማይ ወይም በምድር ወይም በማናቸውም ነገር ቢሆን አትማሉ፤ "አዎ" ቢሆን አዎ ይሁን፤ "አይደለም" ቢሆን አይደለም ይሁን፤ ያለዚያ ይፈረድባችኋል።

## ከእምነት የሆነ ጸሎት

[13]ከእናንተ መካከል በመከራ ውስጥ ያለ አለ? እርሱ ይጸልይ፤ የተደሰተ አለ? የምስ ጋና መዝሙር ይዘምር። [14]ከእናንተ መካከል የታመመ ሰው አለ? የቤተ ክርስቲያን ሽማ ግሌዎችን ይጥራ፤ እነርሱም በጌታ ስም ዘይት ቀብተው ይጸልዩለት። [15]በእምነት የቀረበ ጸሎት የታመመውን ሰው ይፈው ሰዋል፤ ጌታም ያስነሣዋል፤ ኀጢአትም ሠርቶ ከሆነ፣ ይቅር ይባላል። [16]ስለዚህ ኀጢአታችሁን እርስ በርሳችሁ ተናዘዙ፤ ትፈወሱም ዘንድ አንዱ ለሌላው ይጸልይ። የጻድቅ ሰው ጸሎት ኀይል አለው፤ ታላቅ ነገርም ያደር ጋል።

[17]ኤልያስ እንደ እኛ ሰው ነበረ፤ ዝናብ እንዳይዘንብ አጥብቆ ጸለየ፤ በምድርም ላይ ሦስት ዓመት ተኩል ዝናብ አልዘነበም። [18]እንደ ገናም ጸለየ፤ ዝናብም ከሰማይ ዘነበ፤ ምድርም ፍሬዋን ሰጠች።

[19]ወንድሞቼ ሆይ፤ ከእናንተ አንዱ ከእው ነት ቢስትና ሌላው ቢመልሰው፣ [20]ይህን አስተ ውሉ፤ ኀጢአተኛን ከተሳሳተበት መንገድ የሚመልስ ሰው ነፍሱን ከሞት ያድነዋል፤ ብዙ ኀጢአትንም ይሸፍናል።

5፥5 ኤር12፥3፤ 25፥34፤ሕዝ16፥49፤ አሞ6፥1፤ሉቃ16፥19
5፥6 ዕብ10፥38፤ ያዕ4፥2
5፥7 ዘዳ11፥14፤ ኤር5፥24፤ኢል2፥23፤ 1ቆሮ1፥7፤ገላ6፥9
5፥8 1ቆሮ1፥7፤ ሮሜ13፥11
5፥9 መዝ94፥2፤ ማቴ24፥33፤1ቆሮ4፥5፤ ያዕ4፥11፡12፤1ጴጥ4፥5
5፥10 ማቴ5፥12
5፥11 ዘፀ34፥6፤ ዘኍ14፥18፤ኢዩ1፥21፤ 22፤2፥10፤42፥10፡12-17፤ መዝ103፥8፤ማቴ5፥10፤ ዕብ10፥36
5፥12 ማቴ5፥34-37
5፥13 መዝ50፥15፤ ቈላ3፥16
5፥14 መዝ23፥5፤ ኢሳ1፥6፤ማር6፥13፤ 16፥18፤ሉቃ10፥34፤ ሐሥ11፥30
5፥15 ያዕ1፥6 5፥16 ማቴ3፥6፤7፥7፤ዮሐ9፥31፤ ሐሥ19፥18፤ዕብ12፥13፤ 1ጴጥ2፥24
5፥17 1ነገ17፥1፤ ሉቃ4፥25፤ሐሥ14፥15
5፥18 ነገ18፥41-45
5፥19 ማቴ18፥15፤ ያዕ3፥14
5፥20 ሮሜ11፥14፤ 1ጴጥ4፥8

‾5 ወይም ለድግስ

5፥4 *ሁሉን ቻይ…ጌታ፣* የዘፍ 17፥1፤ የ1ሳሙ 1፥3 ማብ ይመ።

5፥5 *በምቾትና በማቀማጠል፣* ሉቃ 16፥19-31 ይመ። ለዕ ርዱ ቀን፤ የፍርድ ቀን ማለት ነው። ክፉዎቹ ባለጠጎች ስለሚመ ጣባቸው ጥፋት ፈጽሞ ደንታ እንደሌላቸውና እስከሚታረዱበት ቀንም ድረስ፣የሚሰቡትን የዕርድ ከብቶች ይመስላሉ።

5፥7 *እንግዲህ፤* ወደ ኋላ ሄዶ ከቍ 1-6 ጋር በማያያዝ ለመን ደርደሪያነት የገባ ቃል ነው። ክርቲያኖች በክፉ ባለጠጎች እጅ መከ ራን እየተቀበሉ ስለሆነ፣ የጌታን ዳግም ምጽአት በትዕግሥት መጠባ በቅ ይኖርባቸዋል። *የፊተኛውንና የኋለኛውን ዝናብም* ፤ በእስራኤል የጸደይ ዝናብ የሚዘንበው ዘር ወዲያውኑ እንደተዘራ በጥቅምትና በኅዳር ሲ ሆን፣ የበልግ ዝናም የሚዘንመው ደግሞ ከመከር በፊት በመጋቢትና በሚያዝያ ነው (ዘዳ11፥14፤ ኤር5፥24፤ ሆሴ 6፥3፤ ኢዮ 2፥24)።

5፥9 *አታጕረምርሙ፤* ያዕቆብ ክርስቲያኖችንም ሆነ ክርስ ቲያን ያልሆኑ ሰዎችን እንዲታገሡ ያሳስባል (ቍ 7-8)። *ፈራጁ በበር ላይ ቆሞአል፣* ይህ የክርስቶስን ዳግም ምጽአት (ቍ 7-8 ይመ)። እንዲሁም በዚያን ጊዜ የሚሆነውን ፍርድ የሚያመለክት ነው። በአዲስ ኪዳን ለምሳሌ ሮሜ13፥12፤ ዕብ 10፥25፤1ጴጥ4፥7፤ራእ 22፥20 ኢየ ሱስ በቶሎ ይመጣል የተባለውን "የመጨረሻዎቹ ቀናት" የጀመሩት ኢየሱስ ወደዚህ ምድር ከመጣበት ጊዜ ጀምሮ ነው፤ ከሚለው ትም ህርት የተነሣ ነው። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ያሉት፤ "የመጨረሻዎቹ ቀናት" (ቍ3) ስለሆኑ፣ አሁን እኛ እየኖርን ያለነው በእነዚህ ቀናት ውስጥ ነው (የዕብ 11 ማብ ይመ)። ይህ መቼ እንደሚሆን አዲስ ኪዳን የሚነግረን ነገር የለም፤ ነገር ግን የምጽአቱ አይቀሬነት አጠያያቂ ስላልሆነ፣ ክርስቲያኖች ምጽአቱን በንቃትና በአንክሮ መጠበቅ ይኖርባቸዋል። እንግዲህ ያዕቆብ የክርስቶስ ዳግም ምጽአት በቅርብ እንደሚሆን የገለጸው ከዚህ የተነሣ ነው።

5፥11 *ኢዮብ እንዴት ታግሦ እንደ ጸና፤* ኢዮብ ታጋሽ ሰው አልነበረም (ኢዮ 3፤ 12፥1-3፤ 16፥1-3፤ 21፥4)፤ ነገር ግን በመከራው ውስጥ ጸንቶ ቆሞአል። (ኢዮ1፥20-22፤ 2፥9-10፤ 13፥15)፤ ምንም እንኳ ኢዮ 5፥13፤ በ1ቆሮ 3፥19 ላይ ቢጠቀስም፣ በአዲስ ኪዳን ውስጥ የኢዮብ ስም የተነሣው እዚህ ስፍራ ብቻ ነው።

5፥12 *አትማሉ፣* ይህ የያዕቆብ ቃል ክርስቶስ ስለዚህ ጕዳይ ካስተማረው ትምህርት ጋር አንድ ዐይነት ነው (ማቴ 5፥33-37)። ያዕቆብ የከለከለው እግዚአብሔር ለአብርሃም እንደ ማለለት ያለውን መሐላ (ዕብ 6፥13) ወይም ቀያፋ ኢየሱስን በመ ሐላ እንዲያዘው ዐይነት የሆነውን (ማቴ 26፥63-64) ወይም ጳውሎስ የተናገረውን (በሮሜ 1፥9፤ እንዲሁም 9፥1) ወይም አንድ ሰው በእግዚአብሔር ፊት የሚያደ ርገውን ዐይነት መሐላ (ዘፀ 22፥11) አይደለም። ያዕቆብ የከለከለው አንድ ሰው የንግግሩን እውነተኛነት ለማስረገጥ ሲል የእግዚአብሔ ርን ስም መጥራትን ወይም በተቀደሰ ነገር መማልን ነው።

5፥14 *ሽማግሌዎች፤* የ1ጢሞ 3፥1፤ 5፥17 ማብ ይመ። *ቤተ ክርስቲያን፤* የማቴ 16፥18 ማብ ይመ። *ዘይት፤* እጅግ ከታወቁት ከጥንቱ ዘመን ፍቱን መድኀኒቶች መካከል አንዱ ነው (ፍቱን መድኀ ኒትነቱን በእስክንድርያ ይኖር የነበረው አይሁዳዊ ምሁር ፊሎ፣ ጲሊኒ እንዲሁም ባለ መድኀኒቱን ጋሌን ጨምሮ በየመጽሐፋቸው ላይ ገልጸዋል፤ እንዲሁም ኢሳ 1፥6፤ ሉቃ 10፥34 ይመ)። አንዳንድ ሰዎች በዚህ ላይ ያዕቆብ ዘይትን የጠቀሰው ከመድኀኒትነቱ አንጻር ነው ሲሉ፣ ሌሎች ደግሞ በእምነት ለሚደረግ ጸሎት ምሳሽ ሆኖ (ቍ 15፤ ማር 6፥13 ይመ) እግዚአብሔር ለሚሰጠው ፈውስ ውጫዊ ምልክት ነው ይላሉ።

5፥17 *ኤልያስ…ጸለየ፤* በ1ነገ 17፥1፤ 18፥41-46 ላይ ኤልያስ የጸለየውን ማለት ነው። ሦስት ዓመት ተኩል (ሉቃ 4፥25 ይመ)፤ የሚለው ቍጥር በ1ነገ 18፥1 መሠረት በማጠ ጋጋት (የሰባት ዓመት ግማሽ) የተገኘ ነው እና ማብራሪያውን (የ1ነገ 18፥1 ማብ ይመ፤ ከራእ 11፥1-6 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥19 *ከእውነት ቢስት፤* ከእውነት የራቀው ሰው አንድም ዝም ብሎ የይስሙላ ክርስቲያን የሆነ (ከዕብ 6፥4-8፤ ከ2ጴጥ 2፥20-21 ጋር ያነጻጽሩ) ወይም በንስሓ መመለስ የሚያስፈልገው በኀጢአት የወደቀ ክርስቲያን ሊሆን ይችላል። በቍ 20 ላይ የተጠቀሰው ሞት የይስሙላ ክርስቲያን ለተባለው "ሁለተኛ ሞት" (ራእ 21፥8) ሲሆን። ለጊዜው በኀጢአት ለወደቀው ክርስቲያን ግን የሥጋ ሞት ነው (ከ1ቆሮ 11፥30 ጋር ያነጻጽሩ። የ1ዮሐ 5፥16 ማብ ይመ።

5፥20 *ብዙ ኀጢአትንም ይሸፍናል፤* ከእውነት የራቀው ሰው ቢመለስ የእግዚአብሔርን ይቅርታ ያገኛል።

# የሐዋርያው ጴጥሮስ መልእክት – አንደኛ

## መግቢያ

### ጸሐፊውና የተጻፈበት ጊዜ

ጸሐፊው ራሱን ሐዋርያው ጴጥሮስ እንደ ሆነ ገልጾአል (1፥1)፤ የመልእክቱም ይዘትና ባሕርይ ጸሐፊው እርሱ መሆኑን የሚደግፍ ነው (የ1፥12፤ 4፥13፤ 5፥1-2፡ 5:13 ማብ ይመ)። በተጨማሪም መልእክቱ በወንጌሎችና በሐዋርያት ሥራ ውስጥ ያሉትን ታሪኮችና ቃላት የጴጥሮስን አባባሎች የሚያንጸባርቁ ናቸው። የመልእክቱ ዋና ሐሳብ፣ ጌታ በምድር ላይ በነበረ ጊዜ፣ በሐዋርያት ዘመን የጴጥሮስ ልምምድና ከሰዎች ጋር የነበረው ኅብረት ምን ይመስል እንደ ነበር የሚያመለክት ነው። ጳውሎስንና መልእክቶቹን እንደሚያውቅም በ2ጴጥ 3፥15-16፤ በገላ 1፥18፤ 2፥1-21 ላይ ተገልጾአል። ስለዚህ ይህ መልእክት ጳውሎስ ከጻፋቸው ደብዳቤዎች ጋር በሐሳብ አንድነትና በአገላለጽ ቢመሳሰል አያስገርምም።

1ኛ ጴጥሮስ ከመጀመሪያው አንሥቶ እምነት የተጣለበት የሐዋርያው የጴጥሮስ ሥራ እንደ ሆነ የታወቀ ነው፤ ይህንንም ጴጥሮስ ቀደም ሲል ጽፎት የነበረውን የመጀመሪያ መልእክቱን በማስታወስ በ2ጴጥ 3፥1 ላይ አመልክቶአል። 1ኛ ቀሌሚንጦስ (95 ዓ.ም.) ከ1ኛ ጴጥሮስ ጋር ዕውቅና አለው። የሐዋርያው ዮሐንስ ደቀ መዝሙር የነበረው ፖሊካርፕ ወደ ፊልጵስዮስ ሰዎች በጻፈው መልእክቱ ውስጥ 1ኛ ጴጥሮስን ተጠቅሞበታል። "የእውነት ወንጌል" ጸሐፊም (140-150) ዓ.ም.) 1ኛ ጴጥሮስን ያውቅ ነበር። በ4ኛው ምእተ ዓመት የነበረው ኢውሳብዮስ ይህ መልእክት በመላው ዓለም ተቀባይነት ያለው መሆኑን አመልክቶአል።

ይህን መልእክት የጻፈው ጴጥሮስ መሆኑን ስለ አዲስ ኪዳን መጻሕፍት ትክክለኛነት የመሰከሩት የጥንት የቤተ ክርስቲያን አባቶች አረጋግጠዋል፤ እነርሱም ኢሬኔዎስ (140-203 ዓ.ም.)፣ ተርቱሊያን (150-222 ዓ.ም.)፤ የእስክንድሪያው ቀሌሚንጦስ (155-215) እና አሪገን (185-253 ዓ.ም.) ናቸው። ስለዚህ መልእክቱ በጴጥሮስ የተጻፈ ለመሆኑ ጥንታዊና ጠንካራ ድጋፍ እንዳለው ከዚህ መረዳት ይቻላል።

### የተጻፈበት ቦታ

ጴጥሮስ የመጀመሪያ መልእክቱን በጻፈበት ጊዜ በባቢሎን ነበር (5፥13)። ባቢሎንን በተመለከተ የተለያዩ ሐሳቦች ቀርበዋል፤ (1) የወታደር ሰፈር የነበረው የግብጻውያን ባቢሎን፣ (2) የመስጴጦማውያን ባቢሎን፣ (3) ኢየሩሳሌም፣ (4) ሮም የሚሉት ይገኙበታል። ጴጥሮስ "ባቢሎን" የሚለውን ስም ልክ እንደ ራእይ መጽሐፍ (የራእ 17፥9-10 ማብ ይመ) በምሳሌነት ሳይጠቀም አይቀርም፤ ጴጥሮስ በመጨረሻው የሕይወት ዘመኑ በሮም እንደ ነበረ በአፈ ታሪክ ተነግሮአል። የጥንት ጸሐፊዎች የመጀመሪያው የጴጥሮስ መልእክት በሮም እንደ ተጻፈ መስክረዋል። በሌላም በኩል ባቢሎን በመጀመሪያው ምእተ ዓመት በኤፍራጠስ ወንዝ አቅራቢያ የምትገኝ ትንሽ ከተማ እንደ ነበረች ታውቆአል። ከዚህም በላይ (1) የራእይ መጽሐፍ እስከ ተጻፈበት ጊዜ ድረስ (95 ዓ.ም.)፣ ባቢሎን የሮም ምሳሌ ሆና መጠቀሷን የሚያመለክት ማስረጃ ያለመኖሩ፣ (2) የ5፥13 ሐሳብ ምሳሌያዊ አነጋገር ወይም ምስጢራዊ ትርጒም ያለው አይደለም የሚሉ ናቸው።

### የመልእክቱ ተደራሲያን

የ1፥1 ማብ ይመ።

### መሪ ሐሳብ

የመጀመሪያው የጴጥሮስ መልእክት አጭር ደብዳቤ ቢሆንም የተለያዩ አስተምህሮችን ያካተተ ነው፤ ስለ ክርስትና ሕይወትና ስለ ክርስቲያናዊ ግዴታዎችም ብዙ ነገሮችን ይዳስሳል። ይህ መልእክት ብዙ የተለያዩ መሪ ሐሳቦች መያዙ የሚያስገርም አይደለም። የተለያዩ አንባቢዎች መጽሐፉ ስለሚናገረው መሪ ሐሳብ የተለያየ አቋም አላቸው። ለምሳሌ ያህል፡- ስለ መለያየት፣ ስለ መከራና ስለ ስደት፣ ስለ መከራና ስለ ክብር፣ ስለ ተስፋ፣ ስለ መናኝ ኑሮና ስለ ድፍረት እንዲሁም ስለ እውነተኛው የእግዚአብሔር ጸጋ ይናገራል ይላሉ። ጴጥሮስ በመልእክቱ፣ አማኞች የቆሙበት ጸጋ እውነተኛ የእግዚአብሔር ጸጋ መሆኑን በመግለጽ "ልመክራችሁና ልመስክርላችሁ" ነው ይላቸዋል (5፥12)። ይህ የደብዳቤው አጠቃላይ መግለጫ ሲሆን፣ ለዋናው ሐሳብ አስተዋፅኦ የሚያደርጉ ጥቃቅን ሐሳቦች እንዳሉም ግልጽ ነው። በተጨማሪም ደብዳቤው ከ1፥13-5፥11 ድረስ በብዙ ዐይነት ምክሮች የተዋቀረ ነው።

### አስተዋፅኦ

1. ሰላምታ (1፥1-2)
2. እግዚአብሔር ስለ ሰጠን ጸጋና ስለ ሰጠን ድነት ማመስገን (1፥3-12)

3. በቅድስና ስለ መኖር የተሰጠ ምክር (1፥3-5፥11)
    - ሀ. የቅድስና መመዘኛ (1፥13-2፥3)
    - ለ. የአማኞች ሰፍራ (ሁነት) (2፥4-12)
        1. መንፈሳዊ ቤት (2፥4-8)
        2. የተመረጠ (ሕዝብ) ትውልድ (2፥9-10)
        3. እንግዶችና መጻተኞች (2፥11-12)
    - ሐ. ለሥልጣን ስለ መገዛት (2፥13-3፥7)
        1. ለገዦች መገዛት (2፥13-17)
        2. ለጌቶች መገዛት (2፥18-20)
        3. ስለ መገዛት የክርስቶስ ምሳሌነት (2፥21-25)
        4. የሚስቶች ለባሎቻቸው መገዛት (3፥1-6)
        5. የባሎች ግዴታ (3፥7)
    - መ. የሁሉም ሰው ግዴታ (3፥8-17)
    - ሠ. የክርስቶስ ምሳሌነት (3፥18-4፥6)
    - ረ. የነገር ሁሉ መጨረሻ ሁኔታ (4፥7-11)
    - ሰ. ስለ ክርስቶስ መከራን የሚቀበሉ ሰዎች ሁኔታ (4፥12-19)
    - ሸ. የሽማግሌዎች ሁኔታ (5፥1-4)
    - ቀ. የወጣቶች ሁኔታ (5፥5-11)
4. የመልእክቱ ዐላማ (5፥12)
5. የመጨረሻ ሰላምታ (5፥13-14)

# 1

የኢየሱስ ክርስቶስ ሐዋርያ ጴጥሮስ፤ በጳንጦስ፥ በገላትያ፥ በቀጰዶቅያ፥ በእስያና በቢታንያ ተበትነው በመጻተኛነት ለሚኖሩ ለእግዚአብሔር ምርጦች፤ [2] እግዚአብሔር አብ አስቀድሞ ካወቃቸው፣ ኢየሱስ ክርስቶስን ለመታዘዝ በደሙ ለተረጩትና በመንፈስ እግካይነት ለተቀደሱት፤

ጸጋና ሰላም ይብዛላችሁ::

## ሕያው ስለ ሆነው ተስፋ ለእግዚአብሔር የቀረበ ምስጋና

[3]የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባትና አምላክ ይባረክ፤ እርሱ ከታላቅ ምሕረቱ የተነሣ በኢየሱስ ክርስቶስ ከሞት መነሣት ምክንያት ለሕያው ተስፋ በሚሆን አዲስ ልደት፣ [4]እንዲሁም በሰማይ ለማይጠፋ፣ ለማይበላሽና ለማይለወጥ ርስት እንደገና ወለደን:: [5]እናንተም በመጨረሻው ዘመን ሊገለጥ የተዘጋጀው ድነት እስኪመጣ ድረስ በእምነት እግካይነት በእግዚአብሔር ኀይል ተጠብቃችኋል:: [6]አሁን በብዙ ዐይነት ፈተና ውስጥ ሆናችሁ ለጥቂት ጊዜ መከራን ብትቀበሉም እንኳ በዚህ እጅግ ደስ ይላችኋል:: [7]እነዚህ ነገሮች በእናንተ ላይ የደረሱት፣ በእሳት ተፈትኖ ቢጠራም፣ ጠፊ ከሆነው ወርቅ ይልቅ እጅግ የከበረው እምነታችሁ እውነተኛ መሆኑ እንደተረጋገጠና ኢየሱስ ክርስቶስ በሚገለጥበት ጊዜ ምስጋናን ክብርንና፥ ውዳሴን እንዲያስገኝላችሁ ነው:: [8]እርሱንም ሳታዩት ትወዱታላችሁ፤ አሁን ባታዩትም በእርሱ ታምናላችሁ መግለጽ በማይቻልና ክብር በሞላበት ሐሤት ደስ ብሎ አችኋል፤ [9]የእምነታችሁን ፍጻሜ እርሱም የነፍሳችሁን ድነት እየተቀበላችሁ ነውና::

[10]ለእናንተ ስለሚሰጠው ጸጋ ትንቢት የተናገሩት ነቢያት ስለዚህ ድነት ተግተው በጥንቃቄ ይመረምሩ ነበር፤ [11]በእነርሱ ውስጥ የነበረው የክርስቶስ መንፈስ ስለ ክርስቶስ መከራ እንዲሁም ከመከራው በኋላ ስለ ሚሆነው ክብር አስቀድሞ በመናገር ያመለከታቸው ጊዜ መቼና እንዴት እንደሚፈጸም ይመረምሩ ነበር:: [12]አሁን ከሰማይ በተላከ መንፈስ ቅዱስ ወንጌልን ባበሠሩላችሁ ሰዎች የነገሯችሁን ነገር ባወሩላችሁ ጊዜ እናንተን እንጂ ራሳቸውን እንዳላገለገሉ ተገለጠላቸው:: መላእክትም እንኳ ሳይቀሩ እነዚህን ነገሮች ይመኛሉ::

## በቅድስና መኖር

[13]ስለዚህ ልባችሁን አዘጋጁ፤ ራሳችሁንም ግዙ፤ ተስፋችሁን ኢየሱስ ክርስቶስ ሲገለጥ

1፥1 ማቴ24፥22፤ ሐሥ2፥9፤16፥6:7፤ 18፥2፤ዕብ11፥13፤ ያዕ1፥1፤2ጴጥ1፥1
1፥2 ቍ14:22፤ ሮሜ1፥7፤8፥29፤ 2ተሰ2፥13፤ ዕብ10፥22፤12፥24
1፥3 ቍ13:21:23፤ ዮሐ1፥13፤1ቆሮ15፥20 2ቆሮ1፥3፤ቲቶ3፥5፤ ዕብ3፥6፤1ጴጥ3፥21
1፥4 ሐሥ20፥32፤ ሮሜ8፥17፤ቆላ1፥5፤ 2ጢሞ4፥8፤1ጴጥ5፥4
1፥5 1ሳሙ2፥9፤ ዮሐ10፥28፤ ሮሜ8፥18፤11፥14
1፥6 ሮሜ5፥2፤ ያዕ1፥2፤1ጴጥ4፥12፤ 5፥10
1፥7 ቍ13፤ ኢዮ23፥10፤ መዝ66፥10፤ ምሳ17፥3፤ ኢሳ48፥10፤ 2ቆሮ4፥17፤1ተሰ2፥19፤ 1ጴጥ4፥13
1፥8 ዮሐ20፥29
1፥9 ሮሜ6፥22
1፥10 ቍ13፤ ማቴ13፥17፤26፥24
1፥11 ማቴ26፥24፤ ሐሥ16፥7፤2ጴጥ1፥21
1፥12 ቍ25፤ ሉቃ24፥49፤ሮሜ4፥24
1፥13 ቍ3:7:10: 21፤ሐሥ24፥25፤ 1ቆሮ1፥7፤ዕብ3፥6

1፥1 *ሐዋርያ፤* የማር 6፥30፤ 1ቆሮ1፥1፤ ዕብ 3፥1 ማብ ይመ:: *ጴጥሮስ፤* ማቴ 16፥18፤ ዮሐ 1፥42 ማብ ይመ:: *በጳንጦስ…በቢታንያ ተበትነው፤* በትንሹ እስያ በየስፍራው ተበትነው ያሉትን፣ ከአይሁድና ከአሕዛብ ወገን የሆኑትን ክርስቲያኖች ይመለከታል:: ከእነዚህ አካባቢ በበዓለ አምሳ ዕለት ብዙ ሰዎች በኢየሩሳሌም ነበሩ (ሐሥ 2፥9-11):: ጳውሎስም፣ በእነዚህ ክፍለ ሀገራት በአንዳንዶቹ ወንጌልን ሰብኮአል፣ አስተምሮአልም (ለምሳሌ:- ሐሥ 16፥6፤ 18፥23፤ 19፥10:26 ይመ):: *በመጻተኛነት፤* ሰለማዊ ቤታቸው በሰማይ የሆነ፣ ነገር ግን በምድር እንግድነት የሚኖሩትን ያመለክታል (ከ1ዜና 29፥15፤ መዝ 39፥12፤ ዕብ 13፥14 ጋር ያነጻጽሩ):: *ምርጦች፤* የኤፌ 1፥4 ማብ ይመ::

1፥2 *በደሙ ለተረጩትና፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ፣ የክርስቶስ የመዋጀት ሥራ ተጠቃሚ ነው (ዘፀ 24፥4-8፤ ኢሳ 52፥15፤ ዕብ 9፥11-14:18-28):: *ኢየሱስ ክርስቶስን ለመታዘዝ* የእግዚአብሔር ምርጫ ወደዚህ ግብ ለማምጣት የታቀደ ነው:: *አብ…ኢየሱስ ክርስቶስን…በመንፈስ፤* ስመዋጀት ሥራ ውስጥ፣ ሦስቱም የሥላሴ አካላት ድርሻ አላቸው:: *ለተቀደሱት፤* የ2ተሰ 2፥13 ማብ ይመ:: የቃላቱ ቅደም ተከተል የሚያሳየው፣ አንድን ሰው ከኀጢአት ወደ ቅድስና ስመመለስ መንፈስ ቅዱስ ያለውን ድርሻ ነው:: *ጸጋና ሰላም፤* የዮና 4፥2፤ ዮሐ 14፥27፤ 20፥19፤ ገላ 1፥3፤ ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ::

1፥3 *በኢየሱስ ክርስቶስ ከሞት መነሣት፤* ሕዝቡ ያገኙትን አዲስ ልደትና እነርሱም እንዲሁ ከሞት እንደሚነሡ ያላቸውን ተስፋ እስተማማኝ ያደርጉላቸዋል:: *ለሕያው ተስፋ፤* በዚህ መልእክት ስለ መከራና ስለ ስደት በተደጋጋሚ ከተጠቀሱት ይልቅ (የቍ 6፤ 2፥12:18-25፤3፥13-18፤ 4፥1:4:12-19፤5፥1: 7-10፣ (ተስፋ የሚለው ቃል እዚህ ላይና በቍ 13:21 ላይ ተጠቅሶአል) ተስፋን ዋና ሐሳብ አድርጎ በውስጡ ስለ ያዘ፣ በመከራ ውስጥ ያለ የተስፋ መልእክት ሊባል ይችላል:: በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ፣ ተስፋ በምኞት ላይ የተመሠረተ ሐሳብ ሳይሆን፣ እንደ እምነት ወደ ፊት ስለሚመጣው ነገር ያስ የሕና ርግጠኛነት ነው::

1፥4 *ርስት፤* እግኖች ጸገም የተወለዱት፣ ተስፋ ለማድረግ ብቻ ሳይሆን፣ የተስፋቸው ዋና መሠረት ለሆነው ርስት ጭምር ነው:: ርስቱም ዘላለማዊና የማይጠፋ ነው፤ እግዚአብሔርም ለእኛ ጠብቆ ይዞልናል::

1፥5 *ድነት፤* የ2ጢሞ 1፥9 ማብ ይመ:: መጽሐፍ ቅዱስ ስለ ድነት ሲናገር፣ 1) እንዳለፈ ሁኔታ፣ ይኸውም:- አንድ ሰው ገና ሲያምን (ቲቶ 3፥5)፣ 2) እንደ አሁን ጊዜ፣ ቀጣይ የቅድስና ሂደት (ቍ 9፤ 1ቆሮ1፥18 ይመ) እና 3) የወደፊት ጊዜ ሲሆን፣ ይህም ክርስቶስ ዳግም ሲመጣ፣ ድነታችን ወይም ቅድስናችን ክብር ስመቀዳጀት፣ ፍጹም በመሆን የሚፈጸምበት ነው (ሮሜ 8፥23:30፤ 13፥11 ይመ):: *በእምነት…በእግዚአብሔር ኀይል፤* የክርስቲያን ጸንቶ መቆም ሁለት ገጽታዎች አሉት፤ ይኸውም፣ በእግዚአብሔር ኀይልና ክርስቲያኑ በእምነት ጸንቶ በመቆም ነው፤ ስለዚህ ከራሱ ፈቃድም ሆነ፣ ከእግዚአብሔር ጥበቃ ውጭ በተጻራሪ ሁኔታ አይደለም::

1፥7 *እምነታችሁ እውነተኛ መሆኑ፤* ሮሜ 5፥3፤ ያዕ 1፥2-4 ይመ:: እምነት ብቻውን የከበረ ሳይሆን፣ የተፈተነ እምነት፣ ዋጋ እንዳለው ጴጥሮስ ተናግሮአል:: *ክብርንና፤* በአንደኛውና በሁለተኛው የጴጥሮስ መልእክቶች ውስጥ ኀይለ ቃል ነው::

1፥8 *አሁን ባታዩትም … ታምናላችሁ፤* ጴጥሮስ እያለ፣ ኢየሱስ ከተናገረው ጋር ተመሳሳይ ነው (ዮሐ 20፥29)::

1፥9 *የነፍሳችሁን፤* የሰውን ሁለንተና ያሳያል::

1፥10 *ነቢያት…በጥንቃቄ ይመረምሩ ነበር፤* በመንፈስ መነዳት፣ ሁሉን ማወቅን እያመለከትም (2ጴጥ 1፥21)፤ ነቢያት የተናገሩት ቃል ምን ማለት እንደ ሆነ፣ አንዳንድ ጊዜ ዐያውቁትም::

1፥11 *የክርስቶስ መንፈስ፤* መንፈስ ቅዱስ በዚህ ስም የተጠራው፣ ክርስቶስ ስለ ላከውና (ዮሐ 16፥7)፣ በእርሱ አገልግሎትም በመገኘቱ ነው:: (ሉቃ 4፥14:18):: *ስለ ክርስቶስ መከራ … ስለሚሆነው ክብር፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ጎልቶ የሚታይ ዐቢይ ሐሳብ ነው (መዝ 22፤ ኢሳ53፥13-52:12፤ ዘካ9፥9-10፤ 13፥7፤ ማቴ 16፥21-23፤ 17፥22፤ 20፥19፤ ሉቃ 24፥26:46፤ ዮሐ 2፥19፤ ሐሥ 3፥17-21፤ ይኸው መሠረታዊ ጽንስ ሐሳብም፣ በዚህ መልእክት ውስጥ ይገኛል (ቍ 18-21፤ 3፥17-22፤ 4፥12-16፤ 5፥1:4:9-10) ከክርስቶስ ጋር ኅብረት ያላቸው ሰዎች ከመከራ በኋላ ክብር ያገኛሉ::

1፥12 *ከሰማይ በተላከ መንፈስ ቅዱስ፤* በበዓለ ኀምሳ፣ ጴጥሮስ በነበረበት ጉባኤ ላይ፣ ክርስቶስ የላከውን መንፈስ ያመለክታል (ሐሥ 2፥33)፤ እግዚአብሔር አብም፣ መንፈስ ቅዱስን ልኮአል (ዮሐ 14፥16:26):: *መላእክትም … ይመኛሉ፤* በግሪክ ቋንቋ ይህ ከፍተኛ የሆነ "የመመርመር" ፍላጎታቸውን የሚያመለክት ነው፤ በተጨማሪም "ዝቅ ብሎ በትኩረት መመልከት" ማለት ነው (ዮሐ 20፥5:11 ይመ)::

1፥13 *ልባችሁን አዘጋጁ፤* በ5፥11 ላይ የሚያበቃው ሰፋ ያለ ምክር፣ የመጀመሪያው ትእዛዝ ይህ ነው:: ይህም ለተግባር የሚያዘጋጅ ስተለዋዋጭ ህይቤ የቀረበ ጥሪ ነው:: እባባሉም፣

ለእናንተ በሚሰጠው ጸጋ ላይ ሙሉ በሙሉ አድርጉ:: [14]ታዛዦች ልጆች እንደ መሆናችሁ መጠን ቀድሞ ባለማወቅ ትኖሩበት የነበረውን ክፉ ምኞት አትከተሉ። [15]ነገር ግን የጠራችሁ እርሱ ቅዱስ እንደ ሆነ እናንተም በኑሮአችሁ ሁሉ ቅዱሳን ሁኑ፤ [16]ምክንያቱም "እኔ ቅዱስ ነኝና እናንተም ቅዱሳን ሁኑ" ተብሎ ተጽፎአል::

[17]ለሰው ሳያደላ በእያንዳንዱ ላይ እንደ የሥራው የሚፈርደውን አባት ብላችሁ የምትጠሩት ከሆነ፣ በዚህ ምድር በእንግድነት ስትኖሩ በፍርሀት ኑሩ:: [18]ከቀድሞ አባቶቻችሁ ከወረሳችሁት ከንቱ ከሆነ ሕይወት የተዋጃችሁት በሚጠፉ ነገር፣ በብር ወይም በወርቅ እንዳልሆነ ታውቃላችሁ፤ [19]ነገር ግን እናንተ የተዋጃችሁት ነውርና እንከን እንደ ሌለበት በግ ደም፣ በክርስቶስ ክቡር ደም ነው:: [20]እርሱ አስቀድሞ የታወቀው ዓለም ከመፈጠሩ በፊት ሲሆን አሁን፣ ግን በመጨረሻው ዘመን ስለ እናንተ ተገለጠ:: [21]በእርሱም አማካይነት፣ ከሞት ባስነሣውና ክብርን በሰጠው በእግዚአብሔር ታምናላችሁ፤ ስለ ዚህ እምነታችሁና ተስፋችሁ በእግዚአብሔር

1፥14 ቍ2:22፤ ሮሜ12፥2፤ኤፌ4፥18
1፥15 ኢሳ35፥8፤ 1ተሰ4፥7፤1ዮሐ3፥3
1፥16 ዘሌ11፥44፡ 45፤19፥2፤20፥7
1፥17 ማቴ6፥9፤ 16፥27፤ሐሥ10፥34፤ ዕብ11፥13፤12፥28
1፥18 ማቴ20፥28፤ 1ቆሮ6፥20፤ገላ4፥3
1፥19 ዘፀ12፥5፤ 1ዮሐ1፥29፤ሮሜ3፥25
1፥20 ማቴ25፥34፤ ኤፌ1፥4፤ዕብ9፥26
1፥21 ቍ3:13፤ ሐሥ2፥24፤ሮሜ 4፥24፤ፊል2፥7-9፤ ዕብ2፥9፤ዕብ3፥6
1፥22 ቍ2:14፤ ዮሐ13፥34፤ ሮሜ12፥10፤ያዕ4፥8
1፥23 ቍ3፤ዮሐ1፥13፤ ዕብ4፥12
1፥25 ኢሳ40፥6-8፤ ያዕ1፥10:11
2፥1 ኤፌ4፥22፤ ያዕ4፥11

ላይ ነው::

[22]እንግዲህ ለእውነት በመታዘዝ ነፍሳችሁን በሳነጻችሁ፣ ለወንድሞቻችሁ ቅን ፍቅር ይኑራችሁ፤ እርስ በርሳችሁም አጥብቃችሁ ከልብ[ሀ] ተዋደዱ:: [23]ዳግመኛ የተወለዳችሁት ከሚጠፋ ዘር ሳይሆን ሕያው በሆነና ጸንቶ በሚኖር፣ በእግዚአብሔር ቃል አማካይነት ከማይጠፋ ዘር ነው:: [24]ምክንያቱም መጽሐፍ እንደሚል፣

"ሥጋ ለባሽ ሁሉ እንደ ሣር ነው፤
ክብሩም ሁሉ እንደ ሜዳ አበባ ነው::
ሣሩ ይጠወልጋል፤ አበባውም ይረግፋል፤
[25]የጌታ ቃል ግን ለዘላለም ጸንቶ ይኖራል::"

የተሰበከላችሁም የምሥራች ቃል ይህ ነው::

**2** እንግዲህ ክፋትን ሁሉ፣ ማታለልን ሁሉ፣ ግብዝነትን፣ ቅናትንና ሐሜትን ሁሉ አስወግዱ፤ [2]በድነታችሁ እንድታድጉ፣ አዲስ እንደ ተወለዱ ሕፃናት ንጹሑን መንፈሳዊ ወተት ተመኙ፤ [3]ጌታ መልካም መሆኑን ቀምሳችኋልና::

[ሀ]22 አንዳንድ የጥናት ቅጆች *ከንጹሕ ልብ* ይላሉ::

2፥2 1ቆሮ3፥2፤ ኤፌ4፥15:16፤ዕብ5፥12:13 2፥3 መዝ34፥8፤ ዕብ6፥5

በመጀመሪያው ክፍለ ዘመን የነበሩ ሰዎች የሚለብሉትን እንደ ቀሚስ ያለውን ረጅም ልብስ ወደ ላይ ሰብስብ በማድረግ፣ ክፌታቸው ለገጠማቸው ተግባር መዘጋጀትን የሚያሳስብ ነው:: *በሚሰጠው ጸጋ* ሙሉ የሆነ በረከትንና ከኀጢአት ነፃ የመውጣትን የመጨረሻ ደረጃ ያመለክታል። ጴጥሮስም፣ የዚህ መልእክት ዋና ዐላማ፣ የእግዚአብሔርን እውነተኛ ጸጋ በሚመለከት ለማበረታታትና ለማረጋገጥ መሆኑን ወደ ፊት ያሳያል (5፥12)::

1፥14 *ልጆች*፤ በእግዚአብሔር ቤተ ሰብ ውስጥ ያሉ ክርስቲያኖች ሁሉ (ቍ 23)፣ የሰማያዊ አባት ልጆች ስለሆኑ (ቍ 17)፣ "በሰማያት የምትኖር አባታችን ሆይ" ብለው መጸለይ ይችላሉ (ማቴ 6፥9):: ክርስቲያኖች የእግዚአብሔር ቤተ ሰብ አባል የመሆን መብት እንደ ተሰጣቸው ተገልጾአል (ሮሜ 8፥15 እና አግራጭ ትርጕሙን ይመ)::

1፥16 *እኔ ቅዱስ ነኝና እናንተም ቅዱሳን ሁኑ*፤ ቅዱስ መሆን ማለት ከኀጢአትና ከርኩሰት ተለይቶ፣ ለእግዚአብሔር መሆን ማለት ነው:: ክፋን ሳለመመልከት፣ ዐይኑ እጅግ ንጹሕ የሆነው እግዚአብሔር ፍጹም ስለሆነ (ዕን 1፥13)፣ ሕዝቡም በምግባሩ ፍጹም እንዲሆን ይፈልጋል:: ይኸኛው የጴጥሮስ መልእክት በተግባር የሚገለጽ ትጋት እንዲኖር፣ የሚመክርና የሚያበረታታ ነው::

1፥17 *ሳያደላ*፤ ሮሜ 2፥11፤ ያዕ 2፥1 ይመ:: *በእንግድነት*፤ የቍ 1 ማብ ይመ *በፍርሀት*፤ መሸበር ሳይሆን፣ ለተቀደስ ሕይወት መሠረት የሆነውን ለእግዚአብሔር ሊደረግ የሚገባውን አክብሮት ያመለክታል (ከምሳ 1፥7፤ 8፥13፤ 16፥6 ጋር ያነጻጽሩ)::

1፥18 *አባቶቻችሁ ከወረሳችሁት ከንቱ ከሆነ ሕይወት*፤ አዲስ ኪዳን በአጽንዖት ስለ አረማውያን ሕይወት ከንቱነት ስለሚናገር፣ አንዳንድ አስተማሪዎች የዚህ መልእክት ተቀባዮች አረማውያን ነበሩ ይላሉ (ሮሜ 1፥21፤ ኤፌ 4፥17)፤ ሌሎች ግን፣ አይሁዳውያን አባቶች በቤታቸው ውስጥ የማስተማር ልማድ ስላላቸው፣ የዚህ መልእክት ተቀባዮች አይሁዳውያን ናቸው ይላሉ፤ የመልእክቱን አጠቃላይ ዐውደ ምንባብ ስንመለከት ግን፣ አይሁዳውያንንም ሆነ አሕዛብን የሚመለከት ሆኖ እናገኘዋለን:: *የተዋጃችሁት*፤ በመጽሐፍ ቅዱስ መዋጀት ማለት፣ የአንድን ሰው ቅጣት በመቀበል ወይም ዕዳውን በመክፈል ነጻ ማውጣት ማለት ነው (ለምሳሌ ዘፀ 21፥30 እና ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዘፀ 13፥13 ይመ):: እንደዚሁም በግሪካውያን ዘንድ፣ ባሪያዎች ራሳቸውን ወይም ሌሎች ሰዎች ስለ እነርሱ ተገቢውን ዋጋ በመክፈል ይዋጁ ነበር:: በተመሳሳይም ኢየሱስ አማኞችን "ከሕግ እርግማን" (ገላ 3፥13) እና "ከክፋት ሁሉ" (ቲቶ 2፥14) ዋጅቶአል:: የተከፈለው ዋጋ፣ ብር ወይም ወርቅ ሳይሆን የክርስቶስ ደም ነው፤ (ኤፌ 1፥7፤ 1ጴጥ 1፥19፤ ራእ 5፥9፤ ማቴ 20፥28፤ ማር 10፥45፤ ዕብ 9፥15) ወይም ክርስቶስ ራሱ ነው (ገላ 3፥13):: ውጤቱም "የኀጢአት ይቅርታ" (የቆላ 1፥14) እና "ጽድቅ" ነው (ሮሜ 3፥24 እና ማብ ይመ)::

1፥19 *ነውርና እንከን እንደሌለበት*፤ ዕብ 9፥14 እና ማብ ይመ:: *በግ*፤ በብሉይ ኪዳን የነበሩት መሥዋዕቶች፣ ፍጹምና ብቸኛ መሥዋዕት ለሆነው ክርስቶስ፣ ምሳሌ ናቸው:: ስለዚህም ክርስቶስ የዓለምን ኀጢአት የሚያስወግድ የፋሲካ በግ ነው (ዮሐ 1፥9፤ 1ቆሮ 5፥7)::

1፥20 *የታወቀው*፤ አንዳንዶች፣ የዚህን ቃል የግሪኩ ትርጕም "አስቀድሞ ማወቅ" ማለት ስለሆነ፣ እግዚአብሔር ከፍጥረት በፊት ሰውን ለማዳን የክርስቶስን አስፈላጊነት ያውቃል ይላሉ (ከራእ 13፥8 ጋር ያነጻጽሩ፤ ስለዚህም ክርስቶስን ላከው:: ሌሎች ደግሞ ከፍጥረት በፊት፣ ክርስቶስ ቤዛ እንዲሆን እግዚአብሔር መርጦታል ለማለት ይተረጕማሉ:: *በመጨረሻው ዘመን*፤ የሐሥ 2፥17፤ 1ጢሞ 4፥1፤ 2ጢሞ 3፥1፤ ዕብ 1፥1፤ የ1ዮሐ 2፥18 ማብ ይመ::

1፥22 *ቅን ፍቅር*፤ ሮሜ 12፥9 ይመ:: *እርስ በርሳችሁም... ተዋደዱ*፤ በዮሐ 13፥34-35 ላይ የተመሠረተ ትእዛዝ ነው:: እንደ ጴጥሮስ፣ ጳውሎስም በ1ተሰ 4፥9-10 ላይ አንባቢዎቹ ስላሳዩት የእርስ በርስ ፍቅር በማመስገን ከዚህም በበለጠ እንዲዋደዱ አበረታትቶአቸዋል:: *ከልብ*፤ በትጋት ማለት ነው::

1፥23 *ዳግመኛ የተወለዳችሁት...በእግዚአብሔር ቃል ... ነው*፤ አዲስ ልደት፣ መንፈስ ቅዱስ በአንድ ሰው ሕይወት ውስጥ በሚሠራው ቀጥተኛ ሥራ አማካይነት ይከናወናል (ቲቶ 3፥5)፤ እንዲሁም የእግዚአብሔር ቃል (ያዕ 1፥18 ይመ) ወንጌልን ለኀጢአተኛ በማቅረብ፣ ንስሓ እንዲገባና በክርስቶስ እንዲያምን የማድረግ ከፍተኛ አስተዋፅኦ አለው:: *ከሚጠፋ ዘር...ጸንቶ በሚኖር*፤ በዚህ ዐውደ ምንባብ፣ ይህ ዘር የማይጠፋ፣ ሕያውና ጸንቶ የሚኖረውን የእግዚአብሔርን ቃል ያመለክታል::

1፥25 *ቃል...ለዘላለም...ይኖራል*፤ የጥቅሱ ዐቢይ ሐሳብ ነው::

2፥1 *እንግዲህ*፤ ይህ ቃል በ1፥23-25 ላይ ከጀመረው ምክር ጋር በማገናኘት፣ "ዳግም የተወለዳችሁት" (1፥23) የሚለውን ሐረግ "አዲስ እንደ ተወለዱ ሕፃናት" (2፥2) ከሚለው ጋር ያነጻጽራል::

2፥2 *እንድታድጉ*፤ ይህ ቃል በግሪክ፣ እድገት ለሕፃናት አስፈላጊ መሆኑን የሚያሳይ ነው:: *መንፈሳዊ ወተት*፤ ምናልባት የእግዚአብሔርን ቃል የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (1፥23:25):: ጸሐፊው የተጠቀመው ዘይቤያዊ አነጋገርን ነው:: ወተት በዚህ ቦታ የተጠቀሰው በ1ቆሮ 3፥2፤ ዕብ 5፥12-14 ላይ እንዳለው ሳይሆን፣ ለሕፃናት የተመጣጠነ ምግብ ሆኖ ነው:: *ተመኙ*፤ የጤነኛ ሕፃን ጽኑ ራብ፣ ለመንፈሳዊ ምግብ አማኞች ሊኖራቸው የሚገባቸውን ብርቱ ፍላጎት በምሳሌ ያሳያል::

2፥3 *ቀምሳችኋልና*፤ የግሪኩ ግስ የሚያመለክተው፣ የመጀ

## ሕያው ድንጋይና የተመረጠ ሕዝብ

[4]በሰው ዘንድ ወደ ተናቀው፣ በእግዚአብሔር ዘንድ ግን ወደ ተመረጠውና ክቡር ወደሆነው ወደዚህ ሕያው ድንጋይ እየቀረባችሁ፣ [5]እናንተ ደግሞ፣ በኢየሱስ ክርስቶስ እማካይነት እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ መንፈሳዊ መሥዋዕት ታቀርቡ ዘንድ፣ ቅዱሳን ካህናት ለመሆን እንደ ሕያዋን ድንጋዮች መንፈሳዊ ቤት ለመሆን ትሠራላችሁ። [6]ምክንያቱም በመጽሐፍ እንዲህ ተብሎ ተጽፎአልና፤

"እነሆ፤ የተመረጠና ክቡር የማእዘን ድንጋይ፣
በጽዮን እኖራለሁ፤
በእርሱም የሚያምን፣ ከቶ አያፍርም።"

[7]እንግዲህ ለእናንተ ለምታምኑት ይህ ድንጋይ ክቡር ነው፤ ለማያምኑት ግን፣

"ግንበኞች የናቁት ድንጋይ፣
እርሱ የማእዘን ራስ[a] ሆነ።"

[8]ደግሞም፣ "ሰዎችን የሚያሰናክል፣
የሚጥላቸውም ዐለት ሆነ።"

የሚሰናከሉት ቃሉን ባለመታዘዛቸው ነው፤ የተመደቡት ለዚህ ነውና።

[9]እናንተ ግን ከጨለማ ወደ አስደናቂ ብርሃኑ የጠራችሁን የእግዚአብሔርን ታላቅ ሥራ እንድታውጁ፣ የተመረጠ ትውልድ፣ የንጉሥ ካህናት፣ ቅዱስ ሕዝብ፣ እግዚአብሔር ለራሱ የለያችሁ ሕዝብ ናችሁ። [10]ቀድሞ የእርሱ ወገን አልነበራችሁም፤ አሁን ግን የእግዚአብሔር ሕዝብ ሆናችኋል፤ ቀድሞ ምሕረትን አላገኛችሁም ነበር፤ አሁን ግን ምሕረትን አግኝታችኋል።

[11]ወዳጆች ሆይ፤ በዚህ ዓለም እንግዶችና መጻተኞች እንደ መሆናችሁ መጠን፣ ነፍስን ከሚዋጋ ሥጋዊ ምኞት እንድትርቁ እለምናችኋለሁ። [12]ምንም እንኳ ክፉ እንደ ምትሠሩ አድርገው ቢያሙችሁም ለፍርድ በሚመጣበት ጊዜ መልካሙን ሥራችሁን ዐይተው እግዚአብሔርን እንዲያከብሩ፣ በአሕዛብ መካከል በመልካም ሕይወት ኑሩ።

2፥4 ቍ7፤ኢሳ42፥1
2፥5 ቍ9፤ዘፀ19፥6፤ ምሳ9፥1፤ኢሳ61፥6፤ 1ቆሮ3፥9፤ኤፌ2፥20-22፤ ፊል4፥18፤1ጢሞ3፥15፤ ዕብ13፥15፤ራእ1፥6፤ 5፥10፤20፥6
2፥6 ኢሳ28፥16፤ ሮሜ9፥32፡33፤ 10፥11፤ኤፌ2፥20
2፥7 ቍ4፤ መዝ118፥22፤ ሐሥ4፥11፤2ቆሮ2፥16
2፥8 ኢሳ8፥14፤ ሉቃ2፥34፤ሮሜ9፥22
2፥9 ቍ5፤ዘፀ19፥6፤ ዘዳ7፥6፤10፥15፤ 1ሳሙ12፥22፤ ኢሳ62፥12፤ ሐሥ26፥18፤ ቲቶ2፥14
2፥10 ሆሴ1፥9፡10፤ 2፥23፤ሮሜ9፥25፡26
2፥11 ሮሜ13፥14፤ 1ቆሮ10፥14፤ገላ5፥16፤ ዕብ11፥13፤ ያዕ4፥1
2፥12 ማቴ9፥8፤ ፊል2፥15፤ቲቶ2፥8፤ 14፤1ጴጥ3፥16

[a]7 ወይም የማእዘን ድንጋይ

መሪያን ቅምሻ ነው፤ ይህ ቅምሻ ተገቢ ውጤት ስላስገኘ፣ አማኞች ተጨማሪ መንፈሳዊ ምግብ እንዲፈልጉ ያስረታታቸዋል።

2፥4 *ሕያው ድንጋይ*፤ ክርስቶስን ነው (ቍ 6-8 እግ ራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ከማቴ 21፥42፤ማር 12፥10-11፤ሉቃ 20፥17፤ ሐሥ 4፥11፤ ሮሜ 9፥33 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይህ ድንጋይም ሕያው ነው፤ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ ስለሆነ በራሱ ሕይ ወት አለው (ዮሐ 1፥4፤ 5፥26)። "የሕይወት ውሃ" (ዮሐ 4፥10-14፤ 7፥38)፣ "የሕይወት እንጀራ" (ዮሐ 6፥51) እና "የሕይወት መን ገድ" (ዕብ 10፥20) የሚለውን ይመ። *በሰው ዘንድ ወደ ተናቀው በእግዚአብሔር ዘንድ ግን ወደ ተመረጠው*፤ በሐዋርያት ሥራ ውስጥም ጴጥሮስ፣ የማያምኑ ሰዎች በኢየሱስ ላይ የሚያስዩ ትን ዐመፅና እግዚአብሔር ኢየሱስን ከፍ ማድረጉን በተደጋጋሚ ገልጾአል (ሐሥ 2፥22-36፤ 3፥13-15፤ 4፥10-11፤ 10፥39-42)።

2፥5 *እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኝ*፤ በእግዚአብሔርና በእኛ መካከል ስሆነው በኢየሱስ ክርስቶስ ሥራ አማካይነት ማለት ነው (ከዮሐ 14፥6 ጋር ያነጻጽሩ)። አማኞች፣ መንፈሳዊ ቤተ መቅደስ የሚሠራባቸው ሕያዋን ድንጋዮችና መንፈሳዊ መሥዋዕትን የሚያቀርቡ፣ ቅዱሳን ካህናት ናቸው። *መንፈሳዊ መሥዋዕት*፤ በአዲስ ኪዳን ልዩ ልዩ የመሥዋዕት ዐይነቶች አሉ፤ እነዚህም፣ ሰውነትን ለእግዚአብሔር ማቅረብ (ሮሜ 12፥1)፣ ገንዘብ ወይም ቁሳቊስ ማቅረብ (ፊል 4፥18፤ ዕብ 13፥16)፣ ለእግዚአብሔር የሚቀርብ የምስጋና መሥዋዕት (ዕብ 13፥15) እና መልካም የማድረግ መሥዋዕት ናቸው (ዕብ 13፥16)። *ቅዱሳን ካህናት*፤ አማኞችን በአጠቃላይ ይመለከታል፤ እንደ ካህናትም አማኞች፦ የእግዚአብሔርንና የእነርሱን ሊቀ ካህን ቅድስና ያንጸባርቃሉ (1፥15፤ ዕብ 7፥26፤ 10፥10 ይመ)፣ መንፈሳዊ መሥዋዕትን ያቀርባሉ (ይህንኑ ቍጥር ይመ)፣ በእግዚአብሔር ፊት ይማልዳሉ በሰው ፊት እግዚአብሔርን ይወክላሉ። *ሕያዋን ድንጋዮች*፤ ቃል በቃል ሲተረጐም አማኞች ድንጋዮች ናቸው ማለት ሳይሆን፣ ስብአዊ ፍጡር ናቸው፤ በተጨ ማሪም የመጡት (ቍ 4)፣ "ሕይወት ሰጭ መንፈስ" (1ቆሮ 15፥45) እና ሕያው ድንጋይ ከሆነው ከክርስቶስ፣ ሕይወት አግኝተው ነው። የድንጋይ ዘይቤያዊ በሆነ አገላለጹ፣ ኢየሱስ በማቴ 16፥18 ላይ ለጴጥሮስ የተናገረውን የሚያንጸባርቅ ሊሆን ይችላሉ። *መንፈሳዊ ቤት*፤ ይህ ቤት ዘይቤያዊ በሆነ አገላለጽ መንፈሳዊ ቢሆንም፣ በእግዚአብሔር መንፈስ የተሠራና የእግዚአብሔር መንፈስ የሚያ ድርበት ነው። ቤቱ የተሠራበት እያንዳንዱ ድንጋይ፣ የከበረ ሕያው ድንጋይ ከሆነው ከኢየሱስ ክርስቶስ ስተሳከው በመንፈስ ቅዱስ፣ ሕያው ሆኖአል (ከሐሥ 2፥33 ጋር ያነጻጽሩ)። በብሉይ ኪዳን የነበረው ቤተ መቅደስ ለዚህ ምንባብ መነሻ መሠረት ሆኖአል (ከዮሐ 2፥19፤ 1ቆሮ 3፥16፤ ኤፌ 2፥19-22 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥6 *ክቡር የማእዘን ድንጋይ*፤ መዝ 118፥22፤ ማቴ 21፥42፤ ማር 12፥10፤ ሉቃ 20፥17፤ ሐሥ 4፥11 ይመ። ከቍ 6-8 ያለው በግልጽ እንደሚያሳየው፣ ይህ ሐረግ ክርስቶስን ያመለክታል። የሕንፃው ንድፍ የሚወሰነው በማእዘኑ ድንጋይ ስለ ሆነ፣ ይህ ድንጋይ በሕንፃው አሠራር ላይ ዋና ቦታ አለው። ጴጥሮስ አማኞችን በሕንፃ መስሎ ያቀርበዋል ("ሕያዋን ድንጋ ዮች" ቍ 5)፤ ይህም ሕንፃ የማእዘኑ ድንጋይ ከሆነው ከክርስቶስ ጋር ተያይዞ የቀረበ ነው። *በእርሱም የሚያምን*፤ የማእዘኑን ድንጋይን በሚመለከት ሁለት እውነታዎች አሉ፦ 1) ጥቂቶች በእርሱ ያምናሉ፤ 2) ሌሎች ደግሞ ይቃወማሉ (ቍ 7)፤ ከዚህም የተነሣ ይሰናከላሉ፣ ይወድቃሉም (ቍ 8)።

2፥8 *የተመደቡትም ለዚህ ነውና*፤ አንዳንዶች ይህን ሐሳብ ለውድቀትና ለጥፋት የተመደቡ ሰዎች እንዳሉ ያመለክታል ይላሉ። ሌሎች ደግሞ እግዚአብሔር ሁሉን ነገር አስቀድሞ በማ ወቅ ችሎታው የሚያምኑትን ስለሚያውቅ፣ የማያምኑ ሰዎች መጨረሻቸው ጥፋት እንዲሆን ወስኖአል ይላሉ (ከ1፥2 ጋር ያነጻ ጽሩ)። ሌሎችም እንዲሁ፣ ጴጥሮስ ያስተላለፈው መልእክት፣ ያለ ማመን ውጤቱ የዘላለም ጥፋት ነው ስማለት ይናገራሉ።

2፥9 *የእግዚአብሔርን ታላቅ ሥራ እንድታውጁ*፤ ኢሳ 43፥20፤ ሐሥ 2፥11 ይመ። *የተመረጠ ትውልድ*፤ ኤፌ 1፥4 እና ማብ ይመ፤ ኢሳ 43፥10፡20፤ 44፥1-2 ይመ። በብሉይ ኪዳን፣ እስራኤላውያን የተመረጠ የእግዚአብሔር ሕዝብ ተብለው እንደ ተጠሩ፣ በአዲስ ኪዳን ደግሞ፣ አማኞች የተመረጡ የእግዚአብሔር ሕዝብ መሆናቸው ተገልጾአል። *የንጉሥ ካህናት*፤ የቍ 5 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ኢሳ 61፥6 ይመ። *ቅዱስ ሕዝብ*፤ ዘዳ 28፥9 ይመ፤ *እግዚአብሔር ለራሱ የለያችሁ ሕዝብ*፤ ዘዳ 4፥20፤ 7፥6፤ 14፥2፤ ኢሳ 43፥21፤ ሚል 3፥17 ይመ። አስቀድሞ የእግዚአብሔር ሕዝብ ባይሆኑም፣ አሁን ግን የእግዚአብሔር ምሕረት አግኝተዋል (ሆሴ 1፥6-10፤ ሮሜ 9፥25-26፤ 10፥19 ይመ)።

*2፥10*፤ የሆሴ 1፥6፡9፤ 2፥1፡22፤ ሮሜ 9፥25-26 ማብ ይመ። በትንቢተ ሆሴዕ እንደተገለጸው፣ እስራኤል የእግዚአብሔር ሕዝብ አይደለም፤ ጳውሎስም በሮሜ መልእክት የሆሴዕን ቃል የተጠ ቀሰው በአሕዛብ ላይ ነው፤ በአንደኛ ጴጥሮስ ግን የቃሉ አጠ ቃቀም ሁለቱንም ሕዝቦች ይመለከታል።

2፥11 *እንግዶችና መጻተኞች*፤ የ1፥1 ማብ ይመ። ዜግነታቸው በሰማይ፣ በመሆኑ በዚህ ምድር እንግዶችና መጻተኞች ናቸው፤ ስለዚህ ከዚህ ዓለም ብሉሽነት ተለይተው፣ ራሳ ቸውን ከኀጢአት ምኞት ሊጠብቁ ይገባቸዋል።

2፥12 *መልካሙን ሥራችሁን ዐይተው*፤ ለዕይታ የሚቀርቡ ሥራዎች፣ መልካም ሊሆኑ ይገባቸዋል (ከማቴ 5፥16 ጋር ያነጻ ጽሩ) "ዐይተው" የሚለው የግሪኩ ቃል፣ ለረጅም ጊዜ በትኩረት ማየት የሚል ትርጕም አለው። አረማውያን የሚሰጡት አስተያ የት "ተራ ፍርድ" አይደለም። *ለፍርድ በሚመጣበት*፤ ምናልባት የፍርድ ቀንን እና ቅጣትን ወይም እግዚአብሔር ሰውን ስማዳን የሚመጣበትን ቀን ያመለክታል። የአማኞች መልካም ኑሮ፣ የማ ያምኑ ሰዎች ንስሐ እንዲገቡና እንዲያምኑ ሊያደርግ ይችላል።

*2፥13-3፥6*፤ ባለሥልጣናት አማኞች ሆኑም አልሆኑ፣ ክርስ ቲያኖች ሕጋዊ ለሆኑ ባለ ሥልጣናት ሁሉ እንዲታዘዙ ጴጥሮስ ያስ ገነዝባል፤ በአግባቡ ለተመሠረተ ሥልጣን፣ ተገቢ ክብሩ መስጠት ለሕዝብ የሚጠቅም ነው፤ የእግዚአብሔርንም ፈቃድ በምድር

## ለአለቆችና ለጌቶች መታዘዝ

[13]ስለ ጌታ ብላችሁ ለምድራዊ ባለ ሥል ጣን ሁሉ ተገዙ፤ የበላይ ባለ ሥልጣን ስለ ሆነ ለንጉሥ ቢሆን፣ [14]ወይም ክፉ አድራጊ ዎችን ለመቅጣት፣ በጎ አድራጊዎችን ለማመ ስገን እርሱ ለሾማቸው ገዦች ታዘዙ፤ [15]ምክ ንያቱም፣ መልካም በማድረግ የአላዋቂዎ ችን ከንቱ ንግግር ዝም እንድታሰኙ የእግዚአ ብሔር ፈቃድ ነው። [16]እንደ እግዚአብሔር አገልጋ ዮች ሆናችሁ በነጻነት ኑሩ እንጂ ነጻነታች ሁን የክፋት መሸፈኛ አታድርጉት። [17]ለሰው ሁሉ ተገቢውን አክብሮት ስጡ፤ ወንድሞችን ውደዱ፤ እግዚአብሔርን ፍሩ፤ ንጉሥን አክብሩ።

[18]እናንተ አገልጋዮች ሆይ፤ ለደጎችና ለገሮች ጌቶቻችሁ ብቻ ሳይሆን ለክፉዎችም በፍጹም አክብሮት ታዘዙ። [19]ስለ እግዚአብሔር ሲል የግፍ መከራን የሚቀበል ሰው ምስጋናን ያገኛል። [20]ክፉ ሥራ ሠርታችሁ ብትቀጡና ብትታገሡ ምን ምስጋና ይኖራችኋል? ነገር ግን መልካም ሥራ ሠርታችሁ መከራ ብትቀ በሉና ብትታገሡ ይህ በእግዚአብሔር ዘንድ ምስ ጋና ያስገኝላችኋል። [21]የተጠራችሁትም ለዚሁ ነው፤ ምክንያቱም ክርስቶስ ስለ እናንተ መከ ራን የተቀበለው የእርሱን ፈለግ እንድትከተሉ ምሳሌን ሊተውላችሁ ነው።

[22]"እርሱ ኀጢአት አላደረገም፤
በአፉም ተንኰል አልተገኘበትም።"

[23]ሲሰድቡት መልሶ አልተሳደበም፤ መከራ ሲደርስበት አልዛተም፤ ነገር ግን በጽድቅ ለሚፈርደው ራሱን አሳልፎ ሰጠ። [24]ለኀጢ አት ሞተን ለጽድቅ እንድንኖር እርሱ ራሱ በሥጋው ኀጢአታችንን በእንጨት መስቀል ላይ ተሸከመ፤ በእርሱ ቍስል እናንተ ተፈውሳ ችኋል። [25]ቀድሞ እንደ ጠፉ በጎች ትቅበዘ በዙ ነበር፤ አሁን ግን ወደ ነፍሳችሁ እረኛና ጠባቂ ተመልሳችኋል።

## በባልና በሚስት መካከል ሊኖር የሚገባ ግንኙነት

**3** ሚስቶች ሆይ፤ እናንተም እንደዚሁ ለባ ሎቻችሁ ተገዙ፤ እንዳንድ ለቃሉ የማይ

2፥13 ሮሜ13፥1፤ ቲቶ3፥1
2፥14 ሮሜ13፥3፡4
2፥15 ቍ12፤1ጴጥ3፥17፤ 4፥19
2፥16 ዮሐ8፥32፤ ሮሜ6፥22፤ገላ5፥13
2፥17 ምሳ24፥21፤ ሮሜ12፥10፤13፥7
2፥18 ኤፌ6፥5፤ ያዕ3፥17
2፥19 1ጴጥ3፥14፡ 17
2፥20 1ጴጥ3፥17
2፥21 ማቴ11፥29፤ 16፥24፤ሐሥ14፥22፤ ሮሜ8፥28፤ፊል1፥29፤ 1ጴጥ3፥9፡18፤4፥1፡13
2፥22 ኢሳ53፥9፤ 2ቆሮ5፥21
2፥23 መዝ9፥4፤ ኢሳ53፥7፤ ሉቃ23፥46፤ ዕብ12፥3፤1ጴጥ3፥9
2፥24 ዘዳ32፥29፤ መዝ103፥3፤ ኢሳ53፥4፡5፡11፤ ዕብ9፥28፤12፥13፤ ያዕ5፥16
2፥25 ኢዩ10፥12፤ኢሳ 53፥6፤ዮሐ10፥11፤3፥1 1ቆሮ7፥16፤ 9፥19፤ ኤፌ5፥22፤1ጴጥ2፥18

ላይ መፈጸም ያበፈልጋል።

2፥13 *ለ ... ባለ ሥልጣናት ሁሉ ተገዙ፤* ባለ ሥልጣናትን የሚሾም እግዚአብሔር ነው (ሮሜ 13፥1-2)። ስለዚህ አንድ ሰው አንድን ባለሥልጣን ባይታዘዝ፣ ባለ ሥልጣናትን የሾመውን እግዚ አብሔርን አልታዘዘም ማለት ነው (ከሮሜ 13፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። *ለንጉሥ፣* ጴጥሮስ ይህን መልእክት በጻፈበት ዘመን የነበረው ገዥ፣ እግዚአብሔርን የማይፈራው ጨካኙ ኔሮ ነበር (ከ54 እስከ 68 ዓ.ም.)። ለንጉሡ ነገሥቱ የሚደረገው መታዘዝ፣ የእግዚአብሔ ርን ሕግና ትእዛዝ ወደ ጐን በመጣል ሊሆን አይገባም (ይህ እን ዴት ተግባራዊ እንደሆነ ለማየት ከሐሥ 4፥19 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥15 *የአላዋቂዎችን ከንቱ ንግግር ዝም እንድታሰኙ፤* የዜግነትን ግዴታ መወጣት፣ በክርስቲያኖች ላይ የሚሰነዘረውን የሐሰት ክስ ከንቱ አድርጎ፣ ወንጌልን ለማያምኑ ሰዎች ለማ ድረስ ዕድል ይሰጣል።

2፥16 *በነጻነት ኑሩ፤* በባለ ሥልጣን ላይ በዐመፅ መነሣትን ሳይሆን፣ እነርሱ አማኞች የእግዚአብሔርን ሕግ እስካልተቃወሙ ድረስ፣ አማኞች ለእግዚአብሔርና ለምድራዊ ባለ ሥልጣናት፣ በነጻነት እንዲገዙ የሚያበረታታ ነው። *የክፋት መሸፈኛ አታድርጉት፤* እውነተኛ ነጻነት እግዚአብሔርን በማገልገልና ለሕግ በመገዛት ላይ የተመሠረተ ነው።

2፥17 *ለሰው ሁሉ ተገቢውን አክብሮት፤* ምክንያቱም ሁሉም ሰው በእግዚአብሔር አምሳል ስለ ተፈጠረ ነው። *እግዚ አብሔርን ፍሩ፤* የ1፥17 ማብ ይመ።

2፥18 *አገልጋዮች፤* ማንኛውንም ዐይነት ሥራ የሚሠሩ፣ በቤት ውስጥ ያሉ አገልጋዮችን ያመለክታል። ዐውደ ምንባቡ እንደሚያመለክተው፣ ጴጥሮስ ይህን የሚናገረው ለክርስቲያን አገልጋዮች ነው። የአዲስ ኪዳን ጸሐፊዎች የባርነትን ሥርዐት ባይቃወሙም (የኤፌ 6፥5 ማብ ይመ)፣ ባርነትን የሚቃወም መርሖዎች አሏቸው። ጴጥሮስ በዚህ ርእስ ላይ ያለው መሠረታዊ ትምህርት፣ በዚህ ዘመን ያለውን የአሠሪና ሠራተኛ ግንኙነት ሊመ ለክት ይችላል (ኤፌ 6፥5-8፤ ቈላ 3፥22-25፤ 1ጢሞ 6፥1-2፤ ቲቶ 2፥9-10 ይመ)።

2፥19 *ስለ እግዚአብሔር ሲል፤* ሕጋዊ ሳልሆነ ሥልጣን "ስለ ጌታ በማለት" መገዛትን ያሳያል (ቍ 13፤ ከኤፌ 6፥7-8 ጋር ያነ ጻጽሩ)፤ ስለዚህም አንድ ሰው የእግዚአብሔር ፈቃድ ከሆነ፣ ያለ አግ ባብ የሆነ መከራን እንኳ ለመቀበል ፈቃደኛ መሆን ይኖርበታል።

2፥21 *የተጠራችሁትም ለዚሁ ነው፤* እግዚአብሔር ለክርስቲያኖች ካለው ዕቅዶች አንዱ፣ ኢፍትሐዊነትን በትዕ ግሥት እንዲያሳልፍ ነው። የእግዚአብሔርም እውነተኛ ጸጋ በዚህ በመልእክት አንዝቢዎች ልምምድ የታየው በዚህ ሁኔታ ነው (5፥12)። *ክርስቶስ ስለ እናንተ መከራን የተቀበለው፤* ከኢሳ 52፥13-53፥12 ጋር ያነጻጽሩ። በጎ ሥራን እየሠሩ፣ ክፉ መከራን የመቀበል ዐይነ ተኛ ምሳሌ ክርስቶስ ነው። መድኀን፣ አገልጋይ በመሆን የተቀበ ለው መከራ፣ ተከታዮቹ የሚቀበሉት መከራ፣ ሥቃይ ሳይሆን እንደ ትልቅ ጥቅም እንዲመለከቱት ያደርጋቸዋል።

*2፥22፤* ቅዱሳት መጻሕፍት፣ ክርስቶስ ኀጢአት እንደሌለበት በግልጽ ተናግረዋል (1፥19፤ ሐሥ3፥14፤ 2ቆሮ5፥21፤ ዕብ4፥15፤7፥26፤ 1ዮሐ 3፥5 ይመ)። *ተንኰል አልተገኘበትም፤* ከቍ 1፤ 3፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

*2፥23፤* ጌታችንን በትዕግሥት መከራን እንዴት እንደተቀበለ በማቴ 27፥12-14፡34-44 እና በተጓዳኝ ምንባቦች ውስጥ ተገልጾአል። *ራሱን አሳልፎ ሰጠ፤* ከ4፥19 ጋር ያነጻጽሩ።

2፥24 *ለኀጢአት ሞተን ለጽድቅ እንድንኖር፤* ከሮሜ 6፥3-14 ጋር ያነጻጽሩ። በቅድስና ለመኖር መስቀልን መሸከም አስፈላጊ እንደሆነ በአጽንዖት ይገልጻል። ክርስቶስ በመስቀል ላይ በመሞቱ፣ አማኞች አዲሱን ሕይወት ይኖሩ ዘንድ፣ ራሳቸውን የጽድቅ መሣሪያ አድርገው ለእግዚአብሔር ለማቅረብ ለኀጢአት ሞተዋል (የሮሜ 6፥11-13 ማብ ይመ)። *ኀጢአታችንን ... ተሸከመ፤* ኢሳ 53፥12 ይመ። ምንም እንኳ ጴጥሮስ፣ ክርስቶስ ምሳሌአችን እንደ ሆነ እያብራራ ቢሆንም፣ አርአያነትን ትቶ ከማለፍ የሚበልጠውን የክ ርስቶስን የመዋጀት ሥራም ጠቅሶአል። ጴጥሮስ ክርስቶስ የእኛ ምትክ በመሆን በመስቀል ላይ ሞቶ እንደዋጀን ጴጥሮስ ይገልጻል። በብሉይ ኪዳን ለመሥዋዕት እንደሚቀርብ በግ፣ ክርስቶስ ምንም በደል ሳይኖርበት ስለ እኛ ሞተ። *መስቀል፤* የሐሥ 5፥30 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ሐሥ 10፥39፤13፥29፤ ገላ 3፥13 ይመ። *እናንተ ተፈውሳችኋል፤* ኢሳ 53፥5 ይመ፤ አንዳንዶች የሥጋ ፈውስ በመዋጀት ሥራ ውስጥ ይጠቃለላል ብለው ቢያምኑም፣ ይህ ክፍል ግን የሥጋ ፈውስን የሚያመለክት አይደለም (ከማቴ 8፥16-17 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ሌሎችም ደግሞ ይህ ክፍል መንፈሳዊ ፈውስን ያመለክታል ይላሉ። ዋናው መልእክት ግን ያክርስቶስ ሞት በእርሱ ለሚያምኑ ሁሉ ድነትን ያስገኛል የሚል ነው።

2፥25 *እረኛና* በዚህ ቦታ የተነሣው ሐሳብ፣ በኢሳ 53 ላይ ከተጠቀሱት ተቅበዝባዥ በጎች ጋር በቀጥታ የሚገናኝ ነው። በጎቹ ከእረኛቸው ተለይተው ይቅበዘበዙ ነበር፤ አሁን ግን ወደ እረኛቸው (ወደ ኢየሱስ) ተመልሰዋል (የመዝ 23፥1፤ ዕብ 13፥20 ማብ ይመ፤ በተጨማሪም ዮሐ 10፥11፡14 ይመ)። *ጠባቂ፤* ክርስቶ ስን ያመለክታል (ከ5፥2፡4፤ ከሐሥ 20፥28 ጋር ያነጻጽሩ)። ሽማ ግሌዎች እረኞችና ጠባቂዎች ስለሆኑ፣ ለእግዚአብሔር መንጋ ሊጠነቀቁ ይገባቸዋል። እረኝነትና ጠባቂነት ሁለት የተ ለያዩ የአገግሎት ዐይነቶች ሳይሆኑ፣ ሁለተኛው የመጀመሪያውን የሚያ ብራራ ነው።

*3፥1-6፤* ለሚስቶች የተሰጠ ትእዛዝ ነው (ከዘፍ 3፥16፤ 1ቆሮ 11፥3፤ ኤፌ 5፥22-24፤ ቈላ 3፥18፤ 1ጢሞ 2፥9-10፤ ቲቶ 2፥5 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥1 *እንደዚሁ* አማኞች ለመንግሥት ባለ ሥልጣናት መገ ዛት እንደሚገባቸውና (2፥13-17) አገልጋዮችም ለጌቶቻቸው መገ ዛት እንዳለባቸው ማለት ነው (2፥18-25)። *ተገዙ፤* በ2፥13፡18 ላይ እንደ ተጠቀሰው ግሪኩ ግስ ሲሆን፣ ለባለ ሥልጣናት መገዛትን ያመለክታል፤ ይሁን እንጂ ይህ ምንባብ፣ የበታችነት ስሜትን አያበረታታም። በቤተ ሰብ ውስጥ ሥርዐት እንዲኖር ከሚያደ ርጉ አስፈላጊ ነገሮች አንዱ መገዛት ነው። *ለቃሉ፤* የወንጌልን

ታዘዙ ቢኖሩ፣ ያለ ቃል በሚስቶቻቸው አኗኗር ተማርከው ይመለሳሉ፤ 2ይህም የሚሆነው ንጹሕና ፍጹም አክብሮት የተሞላውን ኑሮአችሁን ሲመለከቱ ነው። 3ውበታችሁ በውጫዊ ነገሮች በመሽሞንሞን ይኸውም ሹሩባ በመሥራት፣ በወርቅ በማጌጥና በልብስ አይሁን፤ 4ነገር ግን ውበታችሁ በእግዚአብሔር ፊት ዋጋው እጅግ የከበረ፣ ገርና ጭምት መንፈስ ያለበት፣ ምንጊዜም የማይጠፋ የውስጥ ሰውነት ውበት ይሁን። 5ተስፋቸውን በእግዚአብሔር ላይ የጣሉ የቀድሞ ቅዱሳት ሴቶች ራሳቸውን ያስዋቡት በዚህ ዐይነት ለባሎቻቸው በመገዛት ነበርና። 6ሣራም አብርሃምን "ጌታዬ" እያለች ትታዘዘው ነበር፣ እናንተም ምንም ሳትፈሩ መልካም ብታደርጉ የእርሷ ልጆች ናችሁ።

7ባሎች ሆይ፤ እናንተም ደግሞ ጸሎታችሁ እንዳይደናቀፍ በኑሮአችሁ ሁሉ ለሚስቶቻችሁ አስቡላቸው፣ ደካሞች ስለ ሆኑና የሕይወትንም በረከት አብረዋችሁ ስለሚወርሱ አክብሯቸው።

## መልካም በማድረግ መከራን መቀበል

8በመጨረሻም ሁላችሁ በአንድ ሐሳብ ተስማሙ፤ እርስ በርሳችሁ ተሳሰቡ፤ እንደ ወንድማማቾች ተዋደዱ፤ ርኅሩኆችና ትሑታን ሁኑ። 9ክፉን በክፉ ወይም ስድብን በስድብ ፈንታ አትመልሱ፤ በዚህ ፈንታ ባርኩ፤ ምክንያቱም እናንተ የተጠራችሁት እንደነዚህ ያሉትን ነገሮች እያደረጋችሁ በረከትን ለመውረስ ነው። 10ስለዚህ፣

"ሕይወትን የሚወድ፣
 መልካም ቀኖችን ሊያይ የሚፈልግ፣
ምላሱን ከክፉ፣
 ከንፈሮቹንም ተንኰል ከመናገር ይከልክል።
11ከክፉ ይራቅ፤ መልካምንም ያድርግ፤
 ሰላምን ይፈልግ፤ ይከተላትም፤
12ምክንያቱም የጌታ ዐይኖች ጻድቃንን ይመለከታሉና፤
 ጆሮቹም ጸሎታቸውን ለመስማት የተከፈቱ ናቸው፤
የጌታ ፊት ግን በክፉ አድራጊዎች ላይ ነው።"

13መልካም ነገር ለማድረግ ብትቀኑ የሚጐዳችሁ ማን ነው? 14ነገር ግን ስለ ጽድቅ እንኳ መከራ ቢደርስባችሁ ብፁዓን ናችሁ፤ "ዛቻቸውን አትፍሩ*፤ አትታወኩም።" 15ክርስቶስን ጌታ አድርጋችሁ በልባችሁ ቀድሱት። እናንተ ስላላችሁ ተስፋ ምክንያትን ለሚጠይቋችሁ ሁሉ መልስ ለመስጠት ሁል ጊዜ የተዘጋጃችሁ ሁኑ፤ ነገር ግን ይህን ሁሉ በትሕትናና በአክብሮት አድርጉት፤ 16በክርስቶስ ያላችሁን መልካም ጠባይ እከፋፍተው የሚናገሩ ሰዎች በሐሜታቸው እንዲያፍሩ በጎ ኅሊና ይኑራችሁ። 17የእግዚአብሔር ፈቃድ እንዲህ ከሆነ፣ ክፉ ሠርቶ መከራ ከመቀበል ይልቅ መልካም አድርጎ መከራ

3፥3 ኢሳ3፥18-23፤ 1ጢሞ2፥9
3፥4 ሮሜ2፥29፤7፥22፤ ኤፌ3፥16
3፥5 አስ2፥15፤ 1ጢሞ5፥5
3፥6 ዘፍ18፥12
3፥7 ኤፌ5፥25-33፤ ቈላ3፥19
3፥8 ሮሜ12፥10፤ 15፥5፤ኤፌ4፥2፤ 1ጴጥ5፥5
3፥9 ማቴ5፥44፤ ሮሜ8፥28፤ሮሜ 12፥17፤1ተሰ5፥15፤ ዕብ6፥14፤ 1ጴጥ2፥21፡23
3፥12 መዝ34፥12-16
3፥13 ቲቶ2፥14
3፥14 ዮሐ17፤ ኢሳ8፥12፡13፤ 1ጴጥ2፥19፡20፤4፥15፡16
3፥15 ቈላ4፥6፤ ዕብ3፥6
3፥16 ዮሐ21፤ ሐሥ23፥1፤ 1ጴጥ2፥12፡15
3፥17 1ጴጥ2፥15፤ 20፤4፥15፡16፡19

*14 ወይም የሚፈሩትን አትፍሩ

መልእክት ማለት ነው። *ያለ ቃል፡* የማያምኑ ባሎቻቸውን ለክርስቶስ ለመማረክ፣ ክርስቲያን ሚስቶች በመልካም አኗኗራቸው ሊደገፉ ይገባቸዋል።

3፥2 *ንጹሕና ፍጹም አክብሮት፡* ለእግዚአብሔር ካላቸው አክብሮት የተነሣ፣ አኗኗራቸው ሥነ ምግባራዊ ንጽሕናን የተላበሰ ሊሆን ይገባዋል።

3፥3 *ሹሩባ በመሥራት፣ በወርቅ በማጌጥና፤* ቅጥ ያጣ የጠጉር አሠራርንና በጌጣ ጌጥ ማሸብረቅን ያመለክታል። ክርስቲያን ሴቶች ለውበት ብለው ልቅ ለሆነ መጊያጌጥ ልባቸውን ሊሰጡ አይገባም። *ልብስ፡* በግሪኩ የቃሉ ቀጥተኛ ትርጕም "ልብስ" ማለት ቢሆንም፣ በዚህ ዐውደ ምንባቡ መሠረት ግን እጅግ ውድ የሆኑ ልብሶችን የሚያመለክት ነው።

3፥4 *የውስጥ ሰውነት፤* እውነተኛ ውበት በውጫዊ ማሸብረቅ ላይ የተመሠረተ ሳይሆን፣ የባሕርይ ጕዳይ ነው (ኤፌ 3፥16)።

3፥5 *የቀድሞ ቅዱሳት ሴቶች፡* ጴጥሮስ ያቀረባቸው መመዘኛዎች፣ በአንድ የተወሰነ ዘመን ወይም ባሕል ለነበሩ ሴቶች ብቻ አይደለም።

3፥6 *ጌታዬ፡* ይህ ቃል በቊ 1 ላይ እንዳለው መገዛትን የሚያመለክት ነው። *ሳትፈሩ...ልጆች፡* ክርስቲያን ሴቶች፣ ሊገጥማቸው የሚችለውን ጥፋት ለማምለጥ ሳይሆን፣ እንደ ሣራ እግዚአብሔርን በመታመን መልካም ቢያደርጉ፣ የእርሷ ልጆች ይሆናሉ (ከምሳ 3፥25-27 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥7 *ደካሞች ስለ ሆኑና፤* ችግር መቻልን፣ የባሕርይ ጠንካራነትን ወይም የማሰተዋል ችሎታን የሚያመለክት ሳይሆን፣ የአካል ብርታትን የሚገልጽ ነው። *ጸሎታችሁ እንዳይደናቀፍ፡* እግዚአብሔር ስለ ባልና ሚስት የሰጠውን ትእዛዝ ቸል ማለት፣ ከእግዚአብሔርና እርስ በርስ ያለንን መንፈሳዊ ኅብረት ያስተጓጕላል።

*3፥8-12፡* ጴጥሮስ በ2፥11-17 ላይ ለአንባቢዎቹ ሁሉ፣ በ2፥18-25 ለአገልጋዮች፣ በ3፥1-6 ለሚስቶች፣ እንዲሁም በ3፥7 ለባሎች ጽፏል። በዚህ ክፍል፣ አንባቢዎች ሁሉ ከሌሎች ጋር ባላቸው ግንኙነት መልካም ምግባር እንዲኖራቸው ያበረታታቸዋል (በቊ 8 ላይ "ሁላችሁ" የሚለውን ይመ)።

3፥8 *ተስማሙ፤* ሮሜ 12፥16፤ ፊል 2፥2 ይመ። *ተሳሰቡ፤* ሮሜ 12፥15፤ 1ቆሮ 12፥26 ይመ። *እንደ ወንድማማቾች ተዋደዱ፤* 1ተሰ 4፥9-10፤ ዕብ 13፥1 ይመ። *ርኅሩኆችና ... ሁኑ፤* ቈላ 3፥12 ይመ። *ትሑታን ሁኑ፤* ፊል 2፥6-8 ይመ።

*3፥9፤* ሉቃ 6፥27-28፤ ሮሜ 12፥17-21 ይመ።

*3፥10-12፡* ጴጥሮስ ይህን ጥቅስ የወሰደው ከመዝ 34 ሲሆን፣ "ስለዚህ" የሚለውን መስተፃምር በመጠቀም፣ በቍጥር 9 ላይ የቀረበውን ምክር ለመቀበል ምክንያት አድርጎ አቅርቦአል፤ እንደ ባለ መዝሙሩ አገላለጽ ከሆነ፣ 1) እንዲህ ያለውን ነገር የሚያደርግ ሰው፣ ሕይወቱ በደስታ የተሞላ ይሆናል (ቊ 10)፣ 2) የዕድሜውም ዘመን ይረዝማል (ቊ 10)፣ 3) እግዚአብሔርም ሊባርከው ዐይኑን በእርሱ ላይ ያደርጋል (ቊ 12)፣ እንዲሁም 4) የእግዚአብሔር ጆሮዎች የእርሱን ጸሎት ለመስማት የተዘጋጁ ይሆናሉ (ቊ 12)።

3፥13 *የሚጐዳችሁ ማን ነው?* እንደሚታወቀው፣ ሰዎች መልካም ነገር በመሥራታቸው ማንም አይጐዳቸውም፤ በተለይ መልካም ለማድረግ ለሚቀና ሰው ይህ እውነት ነው።

3፥14 *መከራ ቢደርስባችሁ፡* በግሪኩ ይህ ሐረግ፣ ከእውነታ የራቀ ነገርን ያመለክታል። አብዛኛውን ጊዜ ስለ ጽድቅ መከራን መቀበል ባይታይም፣ መከራን ለሚቀበል ሰው ግን፣ ልዩ በረከት ያስገኝለታል (ማቴ 5፥10-12 ይመ)። *ዛቻቸውን አትፍሩ፡* ትርጕሙን ይመ፤ የእግዚአብሔር ሕዝብ፣ በእግዚአብሔር እንደ ማያምኑ ሰዎች ነገሮችን ሲመለከቱ፣ ዓለማዊ አስተሳሰብ ሊኖራቸው ወይም የእግዚአብሔርን ጠላቶች ሊፈሩ አይገባቸውም፤ ይልቁንስ እግዚአብሔርን ብቻ ሊፈሩ ይገባቸዋል (ኢሳ 8፥13)።

3፥15 *ክርስቶስን ጌታ አድርጋችሁ ... ቀድሱት፡* አንባቢዎች ለክርስቶስ ከልባቸው የተሰጡ እንዲሆኑ የቀረበ ምክር ነው፤ ስለ እምነታቸውም እንዲናገሩ ሲጠየቁ የሚሰጡት መልስ እያጡም፤ በስለዚህም መልስ ለመስጠት ዝግጁ ይሆናሉ። *በትሕትናና በአክብሮት፡* ክርስቲያኖች የማያምኑ ሰዎች ቢቃወሙአቸውም፣ ሁል ጊዜ ትሑት ሊሆኑ ይገባቸዋል፤ በተጠየቅን ጊዜ ስለ እምነታችን የምንሰጠው መልስ፣ በፍቅር እንጂ በንቀት የተሞላ ሊሆን አይገባውም።

3፥16 *በሐሜታቸው እንዲያፍሩ፤* በአማኞች ፍቅር የተሞላ አመለካከት፣ የተቃዋሚዎችን መራራነትና ሐሜት ከንቱ መሆኑን አጕልቶ ያሳያል።

መቀበል ይሻላል፤ [18]እንዲሁም ክርስቶስ ለአ ንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ስለ ኀጢአት ሞቶ አልና፤ ወደ እግዚአብሔር ያቀርባችሁ ዘንድ፣ ጻድቅ የሆነው እርሱ ስለ ዐመፀኞች ሞተ፤ እርሱ በሥጋ ሞተ፤ በመንፈስ ግን ሕያው ሆነ፤ [19]በመንፈስም ሄዶ በወህኒ ቤት ለነበሩ ነፍሳት ሰበከላቸው፤ [20]እነዚህ በወህኒ የነበሩት ነፍሳት ቀድሞ በኖኅ ዘመን መርከብ ሲሠራ እግዚአብሔር በትዕግሥት ይጠብቃቸው የነበሩ እምቢተኞች ናቸው፤ በውሃ የዳኑት ጥቂት፣ ይኸውም ስምንት ሰዎች ብቻ ነበሩ። [21]ይህም ውሃ አሁን የጥምቀት ምሳሌ ሆኖ ያድናች ኋል፤ ይህም የሰውነትን እድፍ በማስወገድ ሳይሆን በንጹሕ ኅሊና በእግዚአብሔር ፊት የሚቀ ርብ መማፀኛ[m] ነው፤ የሚያድናችሁም በኢ የሱስ ክርስቶስ ትንሣኤ አማካይነት ነው፤ [22]እርሱም ወደ ሰማይ ወጥቶ በእግዚአብሔር ቀኝ አለ፤ መላእክትና ሥልጣናት፣ ኀይላትም ተገ ዝተውለታል።

3፥18 ሮሜ5፥2፤ ቈላ1፥22፤ዕብ7፥27፤ 1ጴጥ2፥21፤4፥1፤6፥13
3፥19 1ጴጥ4፥6
3፥20 ዘፍ6፥3፡5፡ 13፤14፡8፥18፤ ሮሜ2፥4፤ዕብ11፥7
3፥21 ቍ16፤ ሐሥ22፥16፤ 23፥1፤1ጴጥ1፥3
3፥22 ማቴ28፥18፤ ማር16፥19፤ ሮሜ8፥38፤ዕብ4፥14
4፥1 ሮሜ 6፥18፤1ጴጥ2፥21
4፥2 ሮሜ6፥2፤ 1ጴጥ1፥14
4፥3 ሮሜ13፥13፤ ኤፌ2፥2
4፥4 1ጴጥ3፥16
4፥5 ሐሥ10፥42

## ለእግዚአብሔር መኖር

**4** እንግዲህ ክርስቶስ በሥጋው መከራን ስለ ተቀበለ እናንተም በዚሁ ዐሳብ ታጥ ቃችሁ ተነሡ፤ ምክንያቱም በሥጋው መከራን የሚቀበል ሰው ኀጢአትን ትቶአል። [2]ከዚ ህም የተነሣ ከእንግዲህ በሚቀረው ምድራዊ ሕይ ወት እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ እንጂ እንደ ሥጋ ምኞት አይኖርም። [3]አሕዛብ ፈቅደው እንደሚያደርጉት በመዳራት፣ በሥጋዊ ምኞት፣ በስካር፣ በጭፈራ፣ ያለ ልክ በመጠጣት፣ በእስጸያፊ የጣዖት አምልኮ የተመላለሳችሁ በት ያለፈው ዘመን ይበቃል። [4]ይህን በመ ስለ ብኩን ሕይወት ከእነርሱ ጋር ስለማት ሮጡ እንግዳ ሆኖባቸው በመደነቅ ይሰድ ቧችኋል። [5]ነገር ግን በሕያዋንና በሙታን ላይ ሊፈርድ ለተዘጋጀው መልስ ይሰጣሉ።

[m]21 ወይም ምላሽ

3፥18 *ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ፤* ዕብ 9፥28 ይመ። *ጻድቅ ... ስለ ዐመፀኞች፤* የክርስቲያን ባሕርይ ምን መሆን እንዳለበት ሐዋርያው ጳውሎስ በፊል 2፥5-11 ኢየሱስን ምሳሌ አድርጎ እንዳቀረበው፣ ጴጥሮስም ኢየሱስን እንዲሁ አቅርቦታል። መልካም ነገር በማድረግ መከራን ለመቀበል ዝግጁ ልንሆን ይገባናል (ቍ 13-14፡17)። ጴጥሮስ ስለ ክርስቶስ መከራና ሞት ያለው ሐሳብ፣ ከክርስቶስ የመስቀል ሞት በኋላ ስለሆነው ሁኔታ ሐሳብ እንዲሰጥ አድርጎታል፤ ይኸውም በእስር ቤት ላሉት ነፍሳት ኢየሱስ ወንጌልን ስለ መስበኩና ስለ ጥምቀት ነው (ቍ 19-21 ይመ)። *በመንፈስ ግን ሕያው ሆነ፤* ትንሣኤን ያመለክ ታል። በሌላ ስፍራም፣ ትንሣኤ የእግዚአብሔር አብና (ሐሥ 2፥32፤ገላ1፥1፤ኤፌ1፥20)፣ የእግዚአብሔር ወልድ ድርጊት እንደ ሆነ ተገልጾአል (ዮሐ 10፥17-18)። አማራጭ ትርጕሙ ትክክል ከሆነ፣ ክርስቶስ በራሱ መንፈስ ሕያው ሆኖ፣ በዚሁ መንፈስ "(እርሱ) ሄዶ በወህኒ ቤት ለነበሩ ነፍሳት" ሰብኮላቸዋል ማለት ነው (ቍ 19)።

*3፥19-20ሀ* ለዚህ ክፍል ሦስት ዋና ዋና ትርጓሜዎች ተሰጥተውታል፤ 1) አንዳንዶች፣ ክርስቶስ ሥጋ ከመልበሱ በፊት በኖኅ አማካይነት በዚያን ዘመን ለነበረው ትውልድ እንደ ሰበከ ይናገራሉ፤ 2) ሌሎች ግን፣ ክርስቶስ በሞቱና በትንሣኤው መካከል ባለው ጊዜ ወደ ወኅኒ ሄዶ፣ በኖኅ ዘመን ከሰው ልጆች ጋር ለተጋቡትና ለወደቁት መላእክት ወንጌልን ሰብኮአል ይላሉ (ከዘፍ 6፥1-4፤ 2ጴጥ 2፥4፤ ይሁዳ 6 ጋር ያነጻጽሩ)። በዘፍ 6፥2፡4 ላይ "የእግዚአብሔር ልጆች" የተባሉትም በኢዮ 1፥6፤ 2፥1 ላይ (አማራጭ ትርጕሙን ይመ) የተጠቀሱት መላእክት እንደ ሆኑ ይናገራሉ። ምናልባት ለእነዚህ ክፉ መላእክት የተ ናገረው መልእክት፣ ድል መመታታቸውን የሚመለከት ሊሆን ይችላል፤ 3) ሌሎች ደግሞ፣ ክርስቶስ በሞቱና በትንሣኤው መካከል ባለው ጊዜ፣ ኖኅን ይቃወሙ ለነበሩ ሙታን ወንጌልን እንደ ሰበከላቸው ይናገራሉ፤ የሰበከላቸውም፣ ምናልባት ወንጌልን ወይም ድል መንሣቱንና የሚሰሙትም እንደ ተፈረደባቸው የሚናገር መልእክት ሊሆን ይችላል።

የመጀመሪያው አመለካከት ድክመት፣ በዐውደ ምንባቡ እንደተገለጸው፣ የክርስቶስን ሞትና ትንሣኤ ካገናዘበው ሁኔታ ጋር አያገናኘውም። በሁለተኛው አመለካከት ያለው ዋና ችግር፣ መላእክት ከሴቶች ጋር የጋብቻ ሥጋ ግንኙነት ፈጽሙ ማለቱ ሲሆን፣ መላእክት መናፍስት በመሆናቸው ይህን ዐይነት ተግባር ሊፈ ጽሙ አለመቻላቸውን ባለማጤን ነው። በሦስተኛው አመላካከትም ያለው ዋነኛው ችግር፣ "መንፈስ" የሚለው ቃል የሰዎችን መንፈስ እንደ ሆነ በመቍጠሩ፣ ይህ ቃል መንፈሳዊ ኀይላትን እንደሚያመለክት ዘንግቶአል።

3፥21 *ውሃ...የጥምቀት ምሳሌ ሆኖ፤* በዚህ ቦታ ሁለት ሥዕላዊ መግለጫዎች ቀርበዋል፤ የኖኅ የጥፋት ውሃ ጥምቀትን፣ ጥምቀት ደግሞ ድነትን ያመለክታል። ውሃው ጥምቀትን የሚያሳይ ስለ ሆነ፣ በሁለቱም ሁኔታዎች ስለ ፍርድ (በጥፋት ውሃ የኀጢአተኞችን ሞት፣ በጥምቀት ደግሞ የክርስቶስንና የአ ማኞችን ሞት) ቢናገርም፣ የሚያድን ውሃ ነው። ጥምቀት የድነት ትእምርት በመሆኑ፣ የክርስቶስን ሞት፣ መቀበርና ትንሣኤ ስለሚያሳይ ከእርሱ ጋር አንድ መሆናችንን የሚያመለክት ነው (ሮሜ 6፥4)። *አሁን... ያድናችኋል፤* አማ ኞች፣ ጥምቀት ትእምርት ሆኖ በቀረበበት በክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ ድነዋል። ትእምርቱና እውነታው በትርጕም ተቀራራቢ ከመሆናቸው የተነሣ፣ አንዳንድ ጊዜ ትእምርቱ እውነታውን ለማ ሳየት ይረዳል (የሮሜ 6፥3-4 ማብ ይመ)። *በንጹሕ ኅሊና በእግዚአብሔር ፊት የሚቀርብ መማፀኛ፤* ጥምቀት አማኙ በን ጹሕ ኅሊና የሚፈጽመው ውሳኔ ስለሆነ፣ ጥምቀት በትእምርት የሚያመለክተው እውነት በሕይወቱ ይፈጸማል። *የሚያድናችሁም በኢየሱስ ክርስቶስ ትንሣኤ አማካይነት፤* ሰዎች የሚድኑት፣ የትኛውንም ዐይነት ሃይማኖታዊ ሥርዐት በመፈጸም ሳይሆን በትንሣኤው ኀይል ነው።

3፥22 *ወደ ሰማይ ወጥቶ፤* ሐሥ 1፥9-11 ይመ። *በእግዚ አብሔር ቀኝ፤* ዕብ 1፥3፤ 12፥2 ይመ። *መላእክትና ሥልጣናት፣ ኀይላትም፤* ኤፌ 1፥21፤ 6፥12 ይመ።

4፥1 *እንግዲህ፤* 3፥19-22 በመካከል የገባ ተጨማሪ ሐሳብ ስለ ሆነ፣ 4፥1 በቀጥታ ከ3፥18 የሚቀጥል ነው። በዚህ ምንባብ ውስጥ ስለ ክርስቶስ መከራ ተጠቅሶ የምናገኘው፣ አንድ ሰው በጎ ሥራ በመሥራቱ ያለ አግባብ የሚደርስበትን የመከራ ዐይነት ነው፤ በተጨማሪም መከራው በሥጋ ላይ የሚደርስ ነው ("በሥጋው መከራን ተቀበለ" ቍ 1)። *እናንተም በዚሁ ዐሳብ ታጥቃችሁ ተነሡ፤* አማኞች ያለ አግባብ ሊደርስባቸው የሚችለውን መከራ ለመቀበል ሊዘጋጁና በጎ በማድረግ የሚደርስባቸውን መከራ በመቀበል እንደ ኢየሱስ ዐይነት ትሕ ትና ሊያሳዩ ይገባቸዋል (ፊል 2፥5-11 ይመ)። *ምክንያቱም... ኀጢአትን ትቶአል፤* እንዲህ ያለው መከራ፣ አንድ ሰው ቅድሚያ መስጠት ያለበትን ነገር ያለ ማወላወል እንዲያስቀድም ያስችለዋል፤ የሰው ሕይወት በአደጋ ላይ በሚወድቅበት ጊዜ፣ ቀደም ሲል ትልቅ ቦታ የተሰጣቸው የኀጢአት ምኞቶችና ድርጊ ቶች፣ ዋጋ ቢስ ሆነው ይታዩታል። አማኝ ስለ ክርስቶስ የሚቀበለው ከባድ መከራ፣ ቅድስናን ወደ ፍጹምነት ያሳድገዋል፤ (አንዳንዶች ይህ ምንባብና ጳውሎስ በሮሜ 6፥1-14 ላይ የጻፈው ተመሳሳይነት እንዳላቸው ቢናገሩም፣ ጴጥሮስ ለኀጢአት ስለ መሞት ምንም አልተናገረም)።

4፥2 *እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ...እንደ ሥጋ ምኞት፤* በክርስቶስ ባሕርይ እንደታየው፣ የእግዚአብሔር ፈቃድ ለሕ ይወት ወሳኝ ነው።

4፥3 *አሕዛብ፤* "የጣዖት አምልኮ" የሚለው ቃል፣ ከዚህ መልእክት አንባቢዎች ጥቂቶቹ፣ ከአሕዛብ የኑሮ ዘይቤ የመጡ እንደ ነበሩ ያመለክታል (የ1፥1 ማብ ይመ)። *ያለፈው ዘመን፤* ወደ ክርስቶስ ከመምጣት በፊት ያለውን ጊዜ ያሳያል።

4፥4 *እንግዳ ሆኖባቸው በመደነቅ ይሰድቧችኋል፤* የዚህ መልእክት አንባቢዎች መከራ የተቀበሉበት አንዱ ምክንያት ይህ ነው።

4፥5 *በሕያዋንና በሙታን፤* የመጨረሻው የፍርድ ቀን ሲመጣ የሚኖሩትን ሕያዋንና ሙታን ያመለክታል። *ሊፈርድ ለተ ዘጋጀው፤* በአዲስ ኪዳን፣ እግዚአብሔር አብ እና ወልድ በመጨ ረሻው በታላቁ የፍርድ ቀን እንደሚፈርዱ ተጽፎአል፤ የፍርዱ ባለቤት እግዚአብሔር አብ ቢሆንም፣ ፍርድን እንዲያደርግ ለልጁ ሥልጣን ሰጥቶታል (ከዮሐ 5፥27፤ ሐሥ 17፥31 ጋር ያነጻጽሩ)። *መልስ ይሰጣሉ፤* ሐሥ 17፥31፤ ሮሜ 2፥5፡16 ይመ።

[6]ወንጌል ለሙታን እንኳ ሳይቀር የተሰበከው በዚህ ምክንያት ነው፤ ስለዚህ እንደ ማንኛውም ሰው በሥጋ ይፈረድባቸዋል፤ በመንፈስ ግን እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ ይኖራሉ።

[7]የሁሉ ነገር መጨረሻ ተቃርቦአል፤ ስለዚህ መጸለይ እንድትችሉ ንጹሕ አእምሮ ይኑራችሁ፤ ራሳችሁንም የምትገዙ ሁኑ። [8]ፍቅር ብዙ ኀጢአትን ይሸፍናልና ከሁሉ በላይ እርስ በርሳችሁ ከልብ ተዋደዱ፤ [9]እርስ በርሳችሁ ያለ ማጕረምረም እንግድነት ተቀባበሉ። [10]እንደ ታማኝ የእግዚአብሔር ልዩ ልዩ ጸጋ መጋቢ እያንዳንዱ ሰው በተቀበለው የጸጋ ስጦታ ሌላውን ያገልግል፤ [11]ከእናንተ ማንም የሚናገር ቢኖር እንደ እግዚአብሔር ቃል ይናገር፤ የሚያገለግልም ቢኖር እግዚአብሔር በሚሰጠው ብርታት ያገልግል፤ ይኸውም እግዚአብሔር በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት እንዲከብር ነው፤ ክብርና ኀይል ለእርሱ ከዘላለም እስከ ዘላለም ይሁን፤ አሜን።

## ክርስቲያን በመሆን የሚደርስ መከራ

[12]ወዳጆች ሆይ፤ እንደ እሳት የሚፈትን ብርቱ መከራ በመቀበላችሁ እንግዳ ነገር እንደ ደረሰባችሁ በመቍጠር አትደነቁ፤ [13]ነገር ግን ክብሩ በሚገለጥበት ጊዜ ደስታችሁ ታላቅ እንዲሆን የክርስቶስ መከራ ተካፋዮች በመሆናችሁ ደስ ይበላችሁ። [14]ስለ ክርስቶስ ስም ብትሰደቡ፣ የክብር መንፈስ የሆነው የእግዚአብሔር መንፈስ በእናንተ ላይ ስለሚያርፍ ብፁዓን ናችሁ። [15]ከእናንተ ማንም መከራን የሚቀበል ቢኖር፣ ነፍሰ ገዳይ ወይም ሌባ ወይም ወንጀለኛ ወይም በሰው ነገር ጣልቃ ገቢ ሆኖ መከራን አይቀበል፤ [16]ክርስቲያን በመሆኑ መከራ ቢደርስበት ግን ስለዚህ ስም እግዚአብሔርን ያመስግን እንጂ አይፈር፤ [17]ፍርድ ከእግዚአብሔር ቤት የሚጀምርበት ጊዜ ደርሶአልና። እንግዲህ ፍርድ የሚጀምረው በእኛ ከሆነ ለእግዚአብሔር ወንጌል የማይታዘዙ ሰዎች መጨረሻቸው ምን ይሆን?

[18]እንግዲህ፣

"ጻድቅ የሚድነው በጭንቅ ከሆነ፣
ዐመፀኛውና ኀጢአተኛው እንዴት ሊሆን
ይሆን?"

[19]ስለዚህ እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ መከራ የሚቀበሉ ሁሉ ነፍሳቸውን ለታመኑ ፈጣሪ ዐደራ ሰጥተው መልካም ማድረጋቸውን ይቀጥሉ።

## ለሽማግሌዎችና ለጎልማሶች የተሰጠ ምክር

**5** እንግዲህ ከእነርሱ ጋር እኔም ሽማግሌና የክርስቶስ መከራ ምስክር የሆንሁ እንዲ

4፥6 1ጴጥ3፥19
4፥7 ሐሥ24፥25፤ ሮሜ13፥11
4፥8 ምሳ10፥12፤ ያዕ5፥20፤1ጴጥ1፥22
4፥9 ሮሜ12፥13፤ ፊል2፥14
4፥10 ሮሜ12፥6፡7፤ 1ቆሮ4፥2
4፥11 ሮሜ11፥36፤ 1ቆሮ10፡31፤ኤፌ6፥10፤ 1ጢሞ2፥4
4፥12 1ጴጥ1፥6፡7
4፥13 ማቴ5፥12፡ ሮሜ8፥17፤2ቆሮ1፥5፡ 1ጴጥ1፥7፤5፥1
4፥14 ማቴ5፥11፡ ዮሐ15፥21
4፥16 ሐሥ5፥41
4፥17 ኤር25፥29፤ ሕዝ9፥6፤አሞ3፥2፡ 2ተሰ1፥8፤1ጢሞ3፥15
4፥18 ምሳ11፥31፡ ሉቃ23፥31
4፥19 1ጴጥ2፥15፤ 3፥17
5፥1 ሉቃ24፥48፤ ሐሥ11፥30፤ 1ጴጥ1፥5፡7፤4፥13፤ ራእ1፥9

4፥6 *ለሙታን እንኳ ሳይቀር የተሰበከው፣* ይህ ስብከት ቀድሞ የተከናወነው። ስብከቱ እነዚህ ሰዎች ከሞቱ በኋላ የተደረገ ሳይሆን፣ በሕይወት እያሉ የተደረገ ነበር (ከሞት በኋላ ሰዎች ሊድኑ የሚችሉበት ሌላ ሁኔታ የለም ዕብ 9፥27 ይመ)። *እንደ ማንኛውም ሰው በሥጋ ይፈረድባቸዋል፤* አሁን ሙታን ለሆኑት፣ ወንጌል የተሰበከበት የመጀመሪያው ምክንያት ይህ ነው። አንዳንዶች፣ ይህ ፍርድ በዚህ ሕይወት (ዮሐ 5፥24) ወይም ሊመጣ ባለው ሕይወት (ቍ 5)፣ በሰዎች ሁሉ ላይ እንደሚደርስባቸው ይናገራሉ። በዚህ ምድር ወንጌል ለሰዎች የሚሰበከው፣ በክርስቶስ ሞት አሁን ፍርድን ተቀብለው፣ ሊመጣ ካለው ፍርድ እንዲያመልጡ ነው። ሌሎች ደግሞ፣ እነዚህ ሰዎች የተፈረደባቸው፣ የእግዚአብሔር ሕዝብ ለምን የኀጢአትን ኑሮ እንደማይከተል በማያስተውሉ፣ እንደ ሰው ሐሳብ በሚፈርዱ በአረማውያን ነው ይላሉ (ቍ 2-4 ይመ)። በተመሳሳይ ሁኔታም ዓለም ክርስቶስን አሳወቀውም ነበር (ሐሥ 2፥22-24፡36፤ 3፥13-15፤ 5፥30-32፤ 7፥51-53)። *እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ በመንፈስ ግን፤* አሁን ሙታን ለሆኑት፣ ወንጌል የተሰበከበት ሁለተኛው ምክንያት ይህ ነው። አንዳንዶች ወንጌል የሚሰበከበት ዐላማ፣ የሚሰሙት ሁሉ ከእግዚአብሔር ጋር ለዘላለም እንዲኖሩም ሲሆን፣ ይህን ዘላለማዊ ሕይወት መንፈስ ቅዱስ ይሰጣቸዋል ብለው ያምናሉ። ሌሎች ደግሞ የእግዚአብሔርን ሕዝብ በኀጢአት የተሞላው ዓለም ቢያንላቀላቸውና ቢገድላቸውም፣ ወንጌል የሚሰበከው መንፈስ ቅዱስ የዘላለም ሕይወት ስለሚሰጣቸው ነው ይላሉ።

4፥7 *መጨረሻ ተቃርቦአል፤* የያዕ 5፥9 ማብ ይመ። *ስለዚህ* የመጨረሻው ጊዜ፣ በተለይም የክርስቶስን ዳግም ምጽአት መጠባበቅ የአማኞችን ዝንባሌ፣ ድርጊትና ግንኙነት መልክ ያስይዘዋል (2ጴጥ 3፥11-14)። *መጸለይ፤* ከ3፥7፤ ሉቃ 18፥1፤ 1ቆሮ 7፥5፤ ኤፌ 6፥18፤ 1ተሰ 5፥17፤ ዮሐ 5፥14-15 ጋር ያነጻጽሩ። *ንጹሕ አእምሮ፤* ክርስቲያኖች በአስተሳሰባቸው የበሰለ፣ ጥበብ የተሞላ ውሳኔ ሊሰጡ የሚችሉና በሕይወታቸውም በግልጽ የሚታወቅ ዐይነተኛ ዐላማ ሊኖራቸው ይገባል። *ራሳችሁንም የምትገዙ፤* ገላ 5፥23 ይመ።

4፥8 *ፍቅር ብዙ ኀጢአትን ይሸፍናልና፤* ፍቅር፣ ደግሞ ደጋግሞ ይቅርታ ያደርጋል (ማቴ 18፥21-22፤ 1ቆሮ 13፥5፤ ኤፌ 4፥32 ይመ)። *እርስ በርሳችሁ ከልብ ተዋደዱ፤* 1ተሰ 4፥9-10፤ 2ጴጥ 1፥7፤ 1ዮሐ 4፥7-11 ይመ።

4፥9 *እንግድነት ተቀባበሉ፤* ሮሜ 12፥13፤ 1ጢሞ 3፥2፤ 5፥10፤ ቲቶ 1፥8፤ 3ዮሐ 5-8 ይመ።

4፥10 *እያንዳንዱ ... በተቀበለው የጸጋ ስጦታ፤* ሮሜ 12፥4-8፤ 1ቆሮ 12፥7-11 ይመ።

4፥11፤ *ቃል፤* በግሪኩ ይህ ቃል የሚያመለክተው፣ ቅዱሳት መጻሕፍትን ወይም እግዚአብሔር የተናገረውን ቃል ነው (ሐሥ 7፥38፤ ሮሜ 3፥2 ይመ)። *ክብርና...ለእርሱ...ይሁን፤* 1ቆሮ 1፥26-31፤ ይሁዳ 24-25 ይመ።

4፥12 *ወዳጆች ሆይ፤* ወይም "እናንተ የተወደዳችሁ" ማለት ነው (2፥11 ይመ)። *ብርቱ መከራ በመቀበላችሁ ... አትደነቁ፤* 1፥6-7፤ 2፥20-21 ይመ።

4፥13 *የክርስቶስ መከራ ተካፋዮች በመሆናችሁ ደስ ይበላችሁ፤* የቈላ 1፥24 ማብ ይመ። ጴጥሮስ በአንድ ወቅት፣ ክርስቶስ መከራ ሊቀበል አይገባውም በማለት ተቃውሞ ነበር (ማቴ 16፥21-23)። አማኞች ስለ ክርስቶስ መከራ ሲቀበሉ፣ በጌታ ያላቸውን ደስታ እጅግ ያበዛላቸዋል (ማቴ 5፥10-12፤ ሐሥ 5፥41፤ 16፥25)።

4፥14 *ስለ ክርስቶስ ስም ብትሰደቡ፤* ማቴ 5፥11-12፤ ዮሐ 15፥18-20፤ ሐሥ 5፥41፤ 14፥22፤ ሮሜ 8፥17፤ 2ቆሮ 1፥5፤ ፊል 3፥10፤ 2ጢሞ 3፥12 ይመ።

4፥17 *ፍርድ ከእግዚአብሔር ቤት የሚጀምርበት ጊዜ፤* በአማኞች የሚደርሰው መከራ፣ እግዚአብሔር ሕዝቡን ለማጥራት የሚልከው ፍርድ ነው። *ለእግዚአብሔር ወንጌል የማይታዘዙ ሰዎች መጨረሻቸው ምን ይሆን?፤* እግዚአብሔር በራሱ ሕዝብ ላይ የሚፈርድ ከሆነ፣ በማያምኑት ሰዎች ላይ የሚመጣው ፍርድ ምን ያህል የከፋ እንደሚሆን ያመለክታል።

5፥1 *ከእነርሱ ጋር እኔም ሽማግሌና፤* የሐሥ 20፥17፤ የ1ጢሞ 3፥1፤ 5፥17 ማብ ይመ። በመልእክቱ መጀመሪያ ራሱን እንደ ሐዋርያ ያቀረበው ጴጥሮስ (1፥1)፣ አሁን ደግሞ ራሱን እንደ ሌሎቹ የቤተ ክርስቲያን ሽማግሌዎች ይቈጥራል (ከ2ዮሐ 1፤ 3 ዮሐ 1 ጋር ያነጻጽሩ)። እነዚህ ሽማግሌዎች ካላቸው ታላቅ ኀላፊነትና በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ካለው አስቸጋሪ ሁኔታዎች አንጻር ሲታይ፣ ይህ የጴጥሮስ አባባል እጅግ የሚያበረታታ ነው። እነዚህ ሽማግሌዎች በኀላፊነት የሚመሩአቸው አብያተ ክርስቲያናት በትንሹ እስያ ተበትነዋል (1፥1 ይመ)፤ ጴጥሮስ የአንድ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን መሪ ከሆነ፣ ከእነዚህ ሰዎች እንደ አንዱ የአንድ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን ሽማግሌ ነው ማለት ነው። *የክርስቶስ መከራ ምስክር የሆንሁ፤* ጴጥሮስ ከኢየሱስ አገልግሎት መጀመሪያ አንሥቶ በአገልግሎቱ የተለያዩ ደረጃዎች ሁሉና በመጨረሻው የመከራ ጊዜ ከእርሱ ጋር አብሮ ስለ ነበር፣

ሁም ወደ ፊት የሚገለጠው ክብር ተካፋይ የምሆን በመካከላችሁ ያሉትን ሽማግሌዎች እመክራቸዋለሁ፤ [2]በእናንተ ኀላፊነት ሥር ያለውን የእግዚአብሔርን መንጋ ጠብቁ፤ የምትጠብቁትም ከእግዚአብሔር እንደሚጠበቅባችሁ በግድ ሳይሆን በፈቃደኝነት፣ ለጥቅም በመስገብገብ ሳይሆን ለማገልገል ባላችሁ ጽኑ ፍላጎት ይሁን፤ [3]እንዲሁም በዐደራ ለተሰጣችሁ መንጋ መልካም ምሳሌ በመሆን እንጂ በላያቸው በመሠልጠን አይሁን። [4]የእረኞች አለቃ በሚገለጥበት ጊዜ የማይጠፋውን አክሊል ትቀበላላችሁ።

[5]ጕልማሶች ሆይ፤ እናንተም እንዲሁ ለሽማግሌዎች ተገዙ፤ ሁላችሁም እርስ በርስ በመከባበር ትሕትናን ልበሱ፤ ምክንያቱም፣

"እግዚአብሔር ትዕቢተኞችን ይቃወማል፤

ለትሑታን ግን ጸጋን ይሰጣል።"

[6]ስለዚህ እርሱ በወሰነው ጊዜ ከፍ እንዲያደርጋችሁ ከእግዚአብሔር ብርቱ እጅ በታች ራሳችሁን ዝቅ አድርጉ፤ [7]እርሱ ስለ እናንተ ስለሚያስብ የሚያስጨንቃችሁን ሁሉ በእርሱ ላይ ጣሉት።

[8]ራሳችሁን የምትገዙ ሁኑ፤ ንቁም፤ ጠላታችሁ ዲያብሎስ የሚውጠውን በመፈለግ እንደሚያገሣ አንበሳ ወዲያ ወዲህ ይዞራል።

5፥2 ዮሐ21፥16፤ 2ቆሮ9፥7፤1ጢሞ3፥3፤ ፊሞ14
5፥3 ሕዝ34፥4፤ ማቴ20፥25-28፤ 1ጢሞ4፥12
5፥4 ዮሐ10፥11፤ 1ቆሮ9፥25፤1ጴጥ1፥4
5፥5 ምሳ3፥34፤ ማቴ23፥12፤ኤፌ5፥21፤ 1ጴጥ3፥8
5፥6 ኢዮ5፥11፤ ያዕ4፥10
5፥7 መዝ37፥5፤ 55፥22፤ማቴ6፥25፤ ዕብ13፥5
5፥8 ኢዮ1፥7፤ ሐሥ24፥25፤2ጢሞ4፥17
5፥9 ሐሥ14፥22፤ ቈላ2፥5፤ያዕ4፥7
5፥10 መዝ18፥32፤ ሮሜ8፥28፤2ቆሮ4፥17፤ 2ተሰ2፥17፤ 2ጢሞ2፥10፤1ጴጥ1፥6
5፥11 ሮሜ11፥36
5፥12 ሐሥ15፥22፤ 1ቆሮ16፥13፤ ዕብ13፥22
5፥13 ሐሥ12፥12
5፥14 ሮሜ16፥16፤ ኤፌ6፥23

[9]በዓለም ዙሪያ ያሉት ወንድሞቻችሁ ተመሳሳይ መከራ እንደሚቀበሉ ዐውቃችሁ በእምነት ጸንታችሁ ተቃወሙት።

[10]በክርስቶስ ወደ ዘላለም ክብሩ የጠራችሁ የጸጋ ሁሉ አምላክ፣ ለጥቂት ጊዜ መከራ ከተቀበላችሁ በኋላ እርሱ ራሱ መልሶ ያበረታችኋል፤ አጽንቶም ያቆማችኋል። [11]ኀይል ከዘላለም እስከ ዘላለም ለእርሱ ይሁን፤ አሜን።

## የስንብት ሰላምታ

[12]እንደ ታማኝ ወንድም በምቈጥረው በስልዋኖስ አማካይነት ይህንን አጭር መልእክት ጽፌላችኋለሁ፤ የጻፍሁላችሁም ልመክራችሁና ይህ እውነተኛ የእግዚአብሔር ጸጋ መሆኑን ልመሰክርላችሁ ብዬ ነው። በዚህ ጸጋ ጸንታችሁ ቁሙ።

[13]ከእናንተ ጋር የተመረጠችው፣ በባቢሎን የምትገኘው[m] ሰላምታ ታቀርብላችኋለች፤ እንዲሁም ልጄ ማርቆስ ሰላምታ ያቀርብላችኋል። [14]በፍቅር አሳሳም እርስ በርሳችሁ ሰላምታ ተሰጣጡ።

በክርስቶስ ላላችሁ ለሁላችሁ ሰላም ይሁን።

[m]13 በአንዳንድ ጥንታዊ ቅጆች ላይ *በባቢሎን የምትገኘው ቤተ ክርስቲያን* ይላል።

የእርሱ ምስክር ነው (ከማቴ 26፥58፤ ማር 14፥54፤ ሉቃ 22፥60-62፤ ዮሐ 18፥10-11፡15-16 ጋር ያነጻጽሩ)። በዚህ መልእክት ጴጥሮስ ዐይነተኛ የክርስቶስ መከራ ምስክር ነው (2፥21-24 ይመ)፤ በሐሥ 1፥8 ላይ ያለውን የኢየሱስ ትእዛዝ ፈጽሞአል። *ወደፊት የሚገለጠው ክብር ተካፋይ የምሆን፤* በክርስቶስ አገልግሎት ውስጥ የተገለጠውን ክብር ጴጥሮስ መስክሮአል (ዮሐ 1፥14፤ 2፥11 ይመ)፤ ይኸውም፣ ኢየሱስ በክብር በተለወጠ ጊዜ ስለ ነበረና (ማቴ 16፥27፤ 17፥8) የሚመጣውን የክርስቶስን መንግሥት ክብር ስለ አየነው። እግዚአብሔር በወሰነው ጊዜ፣ ክርስቶስ መከራን ተቀብሎ ወደ ክብሩ እንደ ገባ ሁሉ፣ የእርሱም ሕዝብ መከራ ከተቀበሉ በኋላ፣ ወደ ፊት በሚገለጠው የክርስቶስ ክብር ተካፋዮች ይሆናሉ።

5፥2 *የእግዚአብሔርን መንጋ ጠብቁ፤* ጌታችን የተጠቀመበት ተለዋጭ ዘይቤ ነው (ዮሐ 10፥1-18፤ ሉቃ 15፥3-7)፤ ይህም ዘይቤ፣ በጴጥሮስ ልብ ስፍራ ይዞ ነበር (ዮሐ 21፥15-17፤ ከ1ጴጥ 2፥25 ጋር ያነጻጽሩ)። ጴጥሮስ ይህን መልእክት ሲጽፍ፣ በጎቹን እንዲመግብ ክርስቶስ የሰጠውን ትእዛዝ እየፈጸመ ነበር። ጴጥሮስ ለሽማግሌዎች የጻፈው መልእክት፣ ጳውሎስ ለኤፌሶን ሽማግሌዎች ያደረገውን የስንብት ንግግር ይመስላል (በተለይ ሐሥ 20፥28 ይመ)። "እረኛ" የሚለው ቃል በብሉይ ኪዳንም የሚጠቀስ ተለዋጭ ዘይቤ ነው (ሕዝ 34፥1-10)። *የምትጠብቁትም፤* የዚህ ቃል ተመሳሳይ በሐሥ 20፥28፤ ፊል 1፥1፤ 1ጢሞ 3፥2፤ ቲቶ 1፥7 ላይ ተጠቅሶአል፤ የ1ጢሞ 3፥1 ማብ ይመ። በዚህ ምንባብና በሐሥ 20፥17 ላይ በግልጽ እንደሚታየው፣ "ሽማግሌ"፣ "ጠባቂ" እና "እረኛ" የሚሉት ሦስት ቃላት፣ አንድን የአገልግሎት ዘርፍ ያሚያመለክቱ ናቸው (የቲቶ 1፥7 ማብ ይመ)።

5፥3 *በላያቸው በመሠልጠን አይሁን፤* ከማቴ 16፥24-27፤ ማር 10፥42-45 ፊል 2፥6-11፤ 2ተሰ 3፥9 ጋር ያነጻጽሩ። ጴጥሮስ የሐዋርያነት ሥልጣን ቢኖረውም (ቍ 1 ይመ)፣ በመልእክቱ ውስጥ መልካም ሥነ ምግባርን በምሳሌነት ያቀርባል እንጂ፣ በአንባቢዎች ላይ አልሠለጠነባቸውም።

5፥4 *የእረኞች አለቃ፤* ክርስቶስን ያመለክታል፤ ጻግም በሚመጣበት ጊዜ፣ ለእርሱ በመገዛት በእረኝነት ላገለገሉ ሁሉ ሽልማትን ይሰጣቸዋል። *የማይጠፋውን፤* 1፥4 ይመ። *የማይጠፋውን አክሊል፤* ታማኝ የቤተ ክርስቲያን መሪዎች፣ በምድር ሳሉ ክብር ቢነፈጋቸውም፣ የእረኞች አለቃ ከሆነው ከክርስቶስ በሰማያት ክብርን ይቀበላሉ።

5፥5 *ተገዙ፤* ከ2፥13-3፥6 ድረስ ባለው ክፍል ዐቢይ ሐሳብ ነው። ነገር ግን በዚህ ክፍል፣ የቤተ ክርስቲያንን መሪዎች በሚመለከት ቀርቦአል። *እርስ በርስ በመከባበር ትሕትናን ልበሱ፤* ጴጥሮስ ይህን ሲጽፍ፣ በዮሐ 13 ላይ የተፈጸመው እግር የማጠብ ሁኔታ በሐሳቡ ያለ ይመስላል፤ ምንም እንኳ መጀመሪያ ላይ ኢየሱስ እግሩን እንዳያጥበው ቢከለክለውም፣ አሁን ግን እግር የመታጠብን መልእክት አስተውሎ ጻፈ (ዮሐ 13፥7 ይመ)።

5፥6፤ ሉቃ 14፥11 ይመ። *በወሰነው ጊዜ ከፍ እንዲያደርጋችሁ፤* የእግዚአብሔር ርዳታ የሚገኘው ትክክለኛ በሆነ ጊዜ ነው።

5፥7፤ ከፊል 4፥6-7 ጋር ያነጻጽሩ።

5፥8 *ራሳችሁን የምትገዙ ሁኑ፤* 1ተሰ 5፥6፡8 ይመ። *ንቁም፤* በጌታችን የጌቴሴማኒ የጣር ጊዜ፣ ንቁ አለመሆን ያስከተለውን ችግር፣ ጴጥሮስ ያስታወሰ ይመስላል (ማቴ 26፥36-46)።

5፥9 *ወንድሞቻችሁ፤* ተነጥለው ያሉ ሳይሆኑ፣ መከራ በሚካፈሉበት ኅብረት ውስጥ ናቸው።

5፥10 *የጸጋ፤* የገላ 1፥3፤ ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ።

5፥12 *በስልዋኖስ አማካይነት፤* ይህን መልእክት ወደ ተጻፈላቸው ሰዎች ያደረሰው፣ ስልዋኖስ ሊሆን ይችላል፤ ምናልባትም የጴጥሮስን ሐሳብ በጽሑፍ ያሰፈረው ጸሓፊ እርሱ ሊሆን ይችላል። *ልመክራችሁና...የእግዚአብሔር ጸጋ* በመግቢያ ላይ መሪ ሐሳብ የሚለውን ይመ።

5፥13 *የተመረጠችው፤* የኤፌ 1፥4 ማብ ይመ። *በባቢሎን፤* በመግቢያው ላይ የተጻፈበት ቦታ የሚለውን ይመ። *ልጄ ማርቆስ፤* ለማርቆስ ካለው ቅርበትና ፍቅር የተነሣ ልጄ ብሎ ይጠራዋል። ጴጥሮስ ምናልባት ማርቆስን ወደ ክርስቶስ አምጥቶት ሊሆን ይችላል (1ጢሞ 1፥2 እና ማብ ይመ)።

5፥14 *አሳሳም፤* የ1ቆሮ 16፥20 ማብ ይመ። *በክርስቶስ ላላችሁ ለሁላችሁ ሰላም ይሁን፤* ከክርስቶስ ጋር ኅብረት ላደረጉ ሁሉ፣ መንፈሳዊ ድነትንና በረከትን ማለት ነው። ጴጥሮስ መልእክቱን የሚደመድመው፣ አማኞች ከክርስቶስ ጋር ያላቸውን ኅብረት በመጥቀስ ነው፤ ይህም ሙሉ መልእክቱን ለመረዳት የሚያስችል መሪ ሐሳብ ነው።

# የሐዋርያ ጴጥሮስ መልእክት - ሁለተኛ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ጸሐፊው ራሱ ስምዖን ጴጥሮስ እንደ ሆነ (1፥1) ገልጸአል። የግል ልምዱን በተናገረበት ምንባብ ውስጥም (1፥12-15) አንደኛ መደብ ነጠላ ቊጥር ተውላጠ ስም በመጠቀም፣ ኢየሱስ በተራራ ላይ በክብር በተገለጠ ጊዜ የዐይን ምስክር እንደ ነበረ ተናግሮአል (1፥16-18፤ ከማቴ 17፥1-5 ጋር ያነጻጽሩ)። ጸሐፊው፣ ይህ ሁለተኛ መልእክቱ መሆኑን የተናገረ ሲሆን (3፥1)፣ ጳውሎስን "የተወደደ ወንድማችን" ይለዋል (3፥15 እና ማብ ይመ)። በአጭሩ መልእክቱ የጴጥሮስ ሲሆን የመልእክቱ ባሕርይ ይህንኑ ይደግፋል።

ሁለተኛው የጴጥሮስ መልእክት እንደ አንደኛው መልእክት በመጀመሪያዋ ቤተ ክርስቲያን ዘንድ በስፋት የታወቀና የተረጋገጠ ባይሆንም፣ በመጀመሪያው ምእተ ዓመት መጨረሻና በሁለተኛው ምእተ ዓመት ውስጥ ሥልጣን ያለው መልእክት መሆኑን አምነው በመቀበል የተጠቀሙበት አንዳንዶች አሉ (ቀለሚንጦስ 95 ዓ.ም. ውስጥ ተጠቅሶአል)። ጴጥሮስ መልእክቱን መጻፉ አሪገን እስከ ኖረበት ዘመን ድረስ (185-253 ዓ.ም.) ተቀባይነት አላገኘም ነበር። አሪገንም በዚህ ጉዳይ ጥርጥር እንዳለው ያንጸባርቀ ይመስላል። ኢውሳቢዮስ (265-340) በበኩሉ መልእክቱ በጴጥሮስ እንደ ተጻፈ ቢቀበልም፣ ጥያቄ ውስጥ ካሉት መጻሕፍት ጋር ቈጥሮት ነበር። ከኢውሳቢዮስ በኋላ ግን መጻፉ፣ በቀኖና አጠቃላይ ተቀባይነት አግኝቷል።

### የተጻፈበት ጊዜ

ጴጥሮስ የመጀመሪያውን መልእክት (1ኛ ጴጥሮስ ሊሆን ይችላል) ከጻፈ በኋላ (3፥1)፣ ወደ ሕይወት ዘመኑ መጨረሻ አካባቢ (ከ1፥12-15 ጋር ያነጻጽሩ) ሁለተኛውን መልእክት ጻፈ። የሁለቱም አንባቢያን ተደራስያን አንድ ናቸው። ጴጥሮስ የተሠዋው በኔሮ ዘመነ መንግሥት በመሆኑ መልእክቱን የጻፈው በ68 ዓ.ም. እና በ65 ዓ.ም. መካከል ይሆናል ።

ሁለተኛው የጴጥሮስ መልእክት ከላይ ከተጠቀሰው ጊዜ በኋላ እንደ ተጻፈ የሚናገሩ ቢኖሩም ቅሉ በመልእክቱ ውስጥ ምንም የሚደግፋቸው መረጃ የለም። መልእክቱ የሚዋጋው የስሕተት ትምህርት፣ በመጀመሪያው ምእተ ዓመት ከነበሩት የስሕተት ትምህርቶች ጋር ይመሳሰላል። የመጽሐፉን ሁለተኛ ምዕራፍ በሁለተኛው ምእተ ዓመት ከነበረው ከኖስቲስዝም ጋር እንዲነጻጸር ማድረግ የምዕራፉን ይዘት ከሚፈቅድልን በላይ መለጠጥ ነው። በ2ኛ ጴጥሮስ ውስጥ የተጠቀሱት የስሕተት አስተማሪዎች ከሁለተኛው ምእተ ዓመት መሥራች ኖስቲኮች ጋር የነበሩ ሊሆኑ ስለሚችሉ፣ ከመጨረሻው የጴጥሮስ የሕይወት ዘመን ጋር የማይስማማ ሆኖ ስለ እነርሱ የተጻፈ አንዳች ነገር የለም።

አንዳንድ ሰዎች በ3፥4 ላይ የተጠቀሱት አባቶች የመጀመሪያዪቱ ክርስቲያኖች ናቸው ስለሚሉ ከላይ የተጠቀሰውን ዘመን ወደ ኋላ ይመልሱታል። "አባቶች" የሚለው ቃል ግን ብዙውን ጊዜ የብሉይ ኪዳን አባቶችን የሚያመለክት ነው (ዮሐ6፥31 ሐሥ3፥13፤ ዕብ 1፥1 ጋር ያነጻጽሩ)። እንደዚሁም ስለ ጳውሎስና ስለ መልእክቶቹ የሚናገሩት ክፍሎች (3፥15)፣ ጴጥሮስ ከሞተ በኋላ የነበረውን ዘመን የሚያመለክቱ አይደለም።

### 2ኛ ጴጥሮስና የይሁዳ መልእክት

የጴጥሮስ መልእክትና የይሁዳ መልእክት ግልጽ የሆነ ተመሳሳይነት አላቸው (2ጴጥ ከይሁዳ 4-18 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ግልጽ ልዩነትም አላቸው። አንዱ ከሌላው (ቀድቶአል) ወስዶአል፤ ወይም ሁለቱም ከአንድ የጋራ ምንጭ የተቀዱ ናቸው የሚሉ አሉ። አንዱ ከሌላው ወስዶ ከሆነም ከዋናው ሐሳብ ጋር እንዲጣጣም፣ የደራሲውን ዐላማ እንዲጠናከር እንጂ ለክረጃ ተብሎ አይደለም። ብዙዎች ይሁዳ ጴጥሮስን ተጠቅሞአል ቢሉም፣ ረጅሙ መልእክት (ጴጥሮስ) አጭሩን (ይሁዳ) ተጠቅሞአል ቢባል የበለጠ ይታመናል። እንዲህ ዐይነት መዋዋስ በጥንታውያን የሥነ ጽሑፍ ሥራዎች ውስጥ የተለመደ ነበር። ለምሳሌ ያህል ብዙ ሰዎች ጳውሎስ ፊል 2፥6-11 እና 1ጢሞ3፥16 ሲጽፍ የጥንት መዝሙሮችን ክፍሎች ተጠቅሞ እንደ ነበር ያምናሉ።

### ዐላማው

ጴጥሮስ በመጀመሪያው መልእክቱ ምእመናን ከቤተ ክርስቲያን ውጭ የሚመጣባቸውን ስደት (1ጴጥ 4፥12 ይመ) እንዴት መቋቋም እንደሚገባቸው ይመክራቸዋል፤ በዚህ በሁለተኛው መልእክቱ ግን ወደ ቤተ ክርስቲያን ከገቡት (2፥1፤ 3፥3-4 ይመ) ሐሰተኞች አስተማሪዎችና ከፉዎች እንዴት ራሳቸውን መጠበቅ እንዳለባቸው ያስተምራቸዋል። ሁለቱ መልእክቶች በሐሳብና በይዘት የተለያዩ ቢሆኑም ጴጥሮስ እንደ አንድ የእግዚአብሔር መንጋ እረኛ (ዮሐ21፥15-17)፣ አንባቢዎች ክርስቲያናዊ እምነትንና ተግባርን በማዋሐድ ጤናማ በሆነ አካሄድ እንዲተጉ ያሳስባቸዋል። ዐላማውም በሦስት ይከፈላል፤ (1) የክርስቲያናዊ ሕይወትን እድገት ለማበረታታት (ም1)፤ (2) የስሕተት ትምህርትን ለመዋጋት (ም2)፤ (3) የጌታን ዳግም ምጽአት በመጠባበቅ እንዲበረቱ ለመምከር (ም3) ነው።

**አስተዋፅኦ**

1. **መግቢያ** (1፥1-2)
2. በክርስቲያናዊ በጎ ምግባር ስለ ማደግ የተሰጠ ምክር (1፥3-11)
   ሀ. የመለኮታዊ ኀይል ማስቻል (1፥3-4)
   ለ. ለእድገት የቀረበ ጥሪ (1፥5-7)
   ሐ. የእድገት (ጥቅም) ዋጋ (1፥8-11)
3. የጴጥሮስ መልእክት ዐላማና እውነተኛነት (1፥12-21)
   ሀ. የጻፈበት ዐላማ (1፥12-15)
   ለ. የሥልጣኑ መሠረት (1፥16-21)
4. ከሐሰተኛ መምህራን መጠንቀቅ (ም 2)
   ሀ. መምጣታቸው አስቀድሞ መነገሩ (2፥1-3ሀ)
   ለ. እንደሚፈረድባቸው መረጋገጡ (2፥3ለ-9)
   ሐ. ባሕርያቸው መታወቁ (2፥10-22)
5. የክርስቶስ ዳግም ምጽአት እውነት መሆኑ (3፥1-16)
   ሀ. ጴጥሮስ የጻፈበት ዐላማ መደገሙ (3፥1-2)
   ለ. የዘባቾች መምጣት (3፥3-7)
   ሐ. የክርስቶስ ዳግም ምጽአት እርግጠኛነት (3፥8-10)
   መ. የክርስቶስን ዳግም ምጽአት የተመረኰዙ ምክሮች (3፥11-16)
6. መደምደሚያ አስተያየት (3፥17-18)

**1** የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋይና ሐዋርያ ስምዖን ጴጥሮስ፣ በአምላካችንና በአዳኛችን በኢየሱስ ክርስቶስ ጽድቅ በኩል እንደ ተቀ በልነው ዐይነት ክቡር እምነት ለተቀበሉት፤

²እግዚአብሔርንና ጌታችን ኢየሱስን በማወቅ ጸጋና ሰላም ይብዛላችሁ::

## መጠራትንና መመረጥን ማረጋገጥ

³በገዛ ክብሩና በበጎነቱ የጠራንን እርሱን በማወቅ ለሕይወትና ለእውነተኛ መንፈሳዊነት የሚያስፈልገንን ሁሉ የመለኮቱ ኀይል ሰጥ ቶናል:: ⁴ከክፉ ምኞት የተነሣ በዓለም ካለው ምግባረ ብልሹ ሕይወት አምልጣችሁ ከመለኮታዊ ባሕርይ ተካፋዮች እንድትሆኑ በእነዚህ ነገሮች አማካይነት እጅግ ታላቅና ክቡር የሆነውን ተስፋ ሰጥቶናል::

⁵በዚህም ምክንያት በሙሉ ትጋት በእም ነታችሁ ላይ በጎነትን ለመጨመር ጣሩ፤ በበጎነት ላይ ዕውቀትን፣ ⁶በዕውቀት ላይ ራስን መግዛት፣ ራስን በመግዛት ላይ መጽና ትን፣ በመጽናት ላይ እውነተኛ መንፈሳ ዊነትን፤ ⁷በእውነተኛ መንፈሳዊነት ላይ ወንድ ማዊ መተሳሰብን፣ በወንድማዊ መተሳሰብ ላይ ፍቅርን ጨምሩ:: ⁸እነዚህ ባሕርያት ተትረፍርፈው ቢኖሯችሁ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን በማወቅ ዳተኞችና ፍሬ ቢሶች ከመሆን ይጠብቋችኋል:: ⁹እነዚህ ባሕርያት የሌሉት ግን የሩቁን የማያይ ወይም ዕውር ነው፤ ከቀድሞው ኀጢአቱ መንጻቱንም ረስቶአል::

¹⁰ስለዚህ ወንድሞች ሆይ፤ መጠራታች ሁንና መመረጣችሁን ለማጽናት ከፊት ይልቅ ትጉ፤ ምክንያቱም እነዚህን ብታደርጉ ከቶ አትሰናከሉም፤ ¹¹በዚህም ወደ ጌታችንና አዳኛ ችን ወደ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘላለማዊ መንግ ሥት መግባት በሙላት ይሰጣችኋል::

## የቅዱሳት መጻሕፍት ትንቢት

¹²ስለዚህ ምንም እንኳ እነዚህን ነገሮች ብታውቋቸውና በያዛችሁት እውነት ብት ጸኑም፣ ስለ እነዚህ ነገሮች እናንተን ዘወትር ከማሳሰብ ቸል አልልም:: ¹³በዚህ ምድራዊ ድንኳን ውስጥ እስካለሁ ድረስ እናንተን መቀ ትጐት ትክክል ሆኖ ይታየኛል፤ ¹⁴ምክንያቱም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እንደ ገለጠልኝ ይህን ምድራዊ ድንኳን ቶሎ ጥዬ እንደምሄድ ዐውቃለሁ፤

1፥1 ሮሜ1፥1፤ 3፥21-26፤ቲቶ2፥13፤ 1ጴጥ1፥1
1፥2 ቍ3፡8፤ ሮሜ1፥7፤ፊል3፥8፤ 2ጴጥ2፥20፤3፥18
1፥3 ቍ2፡ ሮሜ8፥28፤1ጴጥ1፥5
1፥4 2ቆሮ7፥1፤ ኤፌ4፥24፤ዕብ12፥ 10፤ ያዕ1፥27፤ 2ጴጥ2፥18-20፤ 1ዮሐ3፥2
1፥5 ቍ2፤ቈላ2፥3
1፥6 ቍ3፡ ሐሥ24፥25፤ ዕብ10፥36
1፥7 ሮሜ12፥10፤ 1ተሰ3፥12
1፥8 ቍ2፤ ዮሐ15፥2፤ ቈላ1፥10፤ቲቶ3፥14
1፥9 ማቴ1፥21፤ ኤፌ5፥26፤ 1ዮሐ2፥11
1፥10 መዝ15፥5፤ ሮሜ8፥28፤2ጴጥ3፥ 17፤ይሁ24
1፥11 መዝ145፥13፤ 2ጢሞ4፥18፤ 2ጴጥ2፥20፤3፥18
1፥12 ፊል3፥1፤ 1ዮሐ2፥21፤ 2ዮሐ2፤ይሁ5
1፥13 ኢሳ38፥12፤2ቆሮ5፥1፡4፤2ጴጥ3፥1
1፥14 ዮሐ13፥36፤ 21፥18፡19፤2ጢሞ4፥6

1፥1 *አገልጋይና፡* የሮሜ 1፥1 ማብ ይመ:: *ሐዋርያ፡* የማር 6፥30፤1ቆሮ1፥1፤ዕብ3፥1 ማብ ይመ:: *ስምዖን ጴጥሮስ፡* የማቴ 16፥18፤ዮሐ 1፥42 ማብ ይመ:: *በአምላካችንና በአዳኛችን በኢ የሱስ ክርስቶስ፡* ኢየሱስ አምላክና አዳኝ እንደ ሆነ የሚያሳይ ነው:: የክርስቶስን አምላክነት የሚያመለክተውን የሮሜ 9፥5 ማብ ይመ:: *እምነት፡* አንድን እውነት ማመን ሳይሆን፣ ከእግዚአብሔር የሚሰጠውን ድነት ለመቀበል በክርስቶስ የመታመንን ችሎታ ነው:: *ለተቀበሉት፡* እግዚአብሔር በጻድቅነቱ የማመንን ችሎታ ለሰዎች ይሰጣል::

1፥2 *እግዚአብሔርንና ጌታችን ኢየሱስን በማወቅ፡* ጴጥሮስ መሠረታዊ የክርስትና አስተምህሮ አስፈላጊነትን በዚህ መልእክት ውስጥ በግልጽ አሳይቶአል(1፥3፡5፡8፤3፥18ይመ):: ጴጥሮስ የስሕ ተት ትምህርት የሆነውን ኑፋቄ ለመቃወም የተጠቀመው፣ የእውነተኛ ዕውቀት አስፈላጊነትን ለክርስቲያኖች በማስተማር ነበር:: *ጸጋና ሰላም፡* የና4፥2፤ዮሐ14፥27፤20፥19፤ገላ1፥3 እንዲ ሁም ኤፌ1፥2 ማብ ይመ::

1፥3 *ክብሩና...በጎነቱ፡* የእግዚአብሔርን ልዕልና የሚያ መለክት ነው፤ "ክብር" የሀልውናውን ልዕልና የሚገልጽ ሲሆን፣ "በጎነት" በተግባር የሚገለጠውን ልዕልናውን ማለትም በሥራ የተገለጠ መልካምነቱን ያመለክታል:: *ለሕይወትና ለእውነተኛ መንፈሳዊነት...የሚያስፈልገንን ሁሉ፡* ለመንፈሳዊ ሕይወት የሚያስፈልገንን ሁሉ፣ እግዚአብሔር እርሱን በማወቅ እንድናገኝ አዘጋጅቶልናል:: በርግጥ ሁለተኛው የጴጥሮስ መልእክት የተጻፈው በሰጋነት ደረጃ የነበረውን የኖስቲሲዝም የስሕተት ትምህርት ለመቃወም ከሆነ፣ ሐዋርያት ያስተላለፉት ዕውቀት ብቻ ለመንፈሳዊ ሕይወት እንደሚያስፈልግና በቂም እንደ ሆነ ሐዋርያው በአጽንዖት ገልጾአል:: ስለዚህም ምስጢራዊ ዕውቀት ለድነት አያስፈልገንም (በ1ዮሐንስ መልእክት መግቢያ ላይ፣ ኖስቲሲዝም የሚለውን ይመ) ::

1፥4 *ከመለኮታዊ ባሕርይ ተካፋዮች እንድትሆኑ፡* ይህ የሚያሳየው ክርስቲያኖች የመለኮትን ተፈጥሮ ይወርሳሉ ማለት ሳይሆን ፣ እግዚአብሔር በመንፈስ ቅዱስ አማካይነት በውስጣቸው እንደሚያድር ብቻ ነው (ዮሐ14፥16-17 ይመ):: የእኛ ሰብእና እንዲሁም ባሕርይ ከጌታ የመለኮት ባሕርይ ጋር ፍጹም ሳይዋሐድ ተለያይቶና ተነጣጥሎ ይኖራል::

*1፥5-9፡* በዚህ ክፍል የተጠቀሱት ምግባራት የፍሬያማ ክርስቲያን ሕይወት የሚያመለክቱ ናቸው::

1፥5 *በእምነታችሁ፡* የክርስትና ሕይወት ሥርና መሠረት ነው (ቍ1 እና ማብ ይመ):: *በጎነትን፡* ከቍ 3 ጋር ያነጻጽሩ:: *ዕው ቀትን፡* የቍ 2-3 ማብ ይመ::

1፥6 *ራስን በመግዛት፡* የሐሰት መምህራን፣ ዕውቀት ራስን የመግዛት አስፈላጊነትን ርባና ቢስ ያደርገዋል ይላሉ፤ ጴጥሮስ ግን፣ ክርስቲያናዊ ዕውቀት ራስን ወደ መግዛት ይመራል ይላል:: *በእውነተኛ መንፈሳዊነት ፡* ከልብ የሆነ እግዚአብሔርን ማክበር ፣ የሕይወትን አቅጣጫ ሁሉ ይቈጣጠራል::

1፥7 *በወንድማዊ መተሳሰብ፡* ለእምነት ቤተ ሰብ አባላት ከልብ የሆነ ፍቅርን፣ ያመለክታል:: *ፍቅርን፡* በገለኝነት ላይ ያልተመሠረተ፣ ለሌሎች ጥቅም ሲባል ራስን መሥዋዕት እስከ ማድረግ የሚያደርስ ተነሣሥቶት ነው (የ1ጴጥ 4፥8 ማብ ይመ)::

1፥8 *እነዚህ ባሕርያት...ቢኖሯችሁ፡* ጴጥሮስ፣ በዚህ ቍጥር የተዘረዘሩትን ባሕርያት በቅደም ተከተል ከአንዱ ወደ ሌላው እንዲኖሩን ማለቱ አይደለም:: *በብዛት፡* ጴጥሮስ ይህን ሲል፣ የማያቋርጠውን መንፈሳዊ ዕድገት በማሰብ ነው:: *በማወቅ፣.... ፍሬ ቢሶች ከመሆን ይጠብቋችኋል፡* የአንድ ክርስቲያን ዕውቀት የአኗኗር ሁኔታውን መለወጥ አለበት:: የኖስቲሲዝም የስህተት ትምህርት ተከታዮች እንደሚያስተምሩት፣ ዕውቀት በዘፈቀደ እንድንመላለስ ሊያደርገን አይችልም፤ ይልቁንም የቅድስናና የሌሎች በጎ ተግባራት ሕይወት እንዲኖረን ያደርጋል (ከቈላ 1፥9-12 ጋር ያነጻጽሩ)::

1፥9 *የሩቁን የማያይ ወይም ዕውር፡* ምናልባት ጴጥሮስ "የሩቁን የማያይ" ሲል "ዐይኑን የጨፈነ" የሚለውን አማራጭ ትርጒም በሐሳቡ ይዞ ሊሆን ይችላል፣ እንደዚህ ያለው ሰው፣ እውነትን ላለመቀበል ዐይኑን የጨፈነ ዕውር ነው::

1፥10 *መጠራታችሁንና መመረጣችሁን ለማጽናት፡* ከቍ5-7 ያሉትን መልካም ባሕርያት በመላበስ እነርሱም ሆኑ ሌሎች፣ እግዚ አብሔር እንደ ጠራቸውና እንደ መረጣቸው እርግጠኞች ሊሆኑ ይችላሉ (ከማቴ7፥20 ጋር ያነጻጽሩ):: እውነተኛ እምነት እንዳላቸው የሚታወቀውም በጎ የሆኑ ፍሬዎች አፍርተው ሲገኙ ብቻ ነው (ከገላ5፥6፤ያዕ2፥18 ጋር ያነጻጽሩ):: እግዚአብሔር የመረ ጣቸውና የጠራቸው እንዲታዘዙትና በቅድስናም እንዲኖሩ ነው (1ጴጥ1፥2፤ኤፌ1፥3-6)፤ እነዚህ ፍሬዎችም ፣ የአምላክ መሆ ናቸውን ያረጋግጣሉ:: *አትሰናከሉም፡* በዚህ መንገድ እምነታቸው እውነተኛ መሆኑን የሚያስመሰክሩ ሁሉ ፣ ጸንተው ይኖራሉ እንጂ አይሰናከሉም::

1፥11 *ዘላለማዊ መንግሥት፡* የዘላለም ሕይወት ማለት ነው (ከማቴ25፥46 ጋር ያነጻጽሩ):: *ሙላት ይሰጣችኋል፡* ይህ የሚገኘው፣ ጴጥሮስ ያዘዛቸውን ፍሬ ሲያፈሩ ነው (ቍ5-10 ይመ)::

1፥13 *በዚህ...ድንኳን፡* በግሪኩ "ሰውነት" የሚለው ቃል ድንኳን ማለትም ነው (ዮሐ1፥14 እና 2ቆሮ5፥1 እና ማብ ይመ::)

1፥14 *ክርስቶስ እንደ ገለጠልኝ፡* ምናልባት በዮሐ21፥18-19 ላይ የተጠቀሰው ወይም ከዚያ በኋላ ያገኘው ሌላ መገለጥ ሊሆን ይችላል::

[15]እነዚህን ነገሮች ከተለየኋችሁም በኋላ ዘወትር ታስቡ ዘንድ እተጋለሁ።

[16]ስለ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ኃይልና ስለ *መምጣቱ* የነገርናችሁ እኮ የእርሱን ግርማ በዐይናችን አይተን እንጂ፣ በበዎች ጥበብ የተፈጠረውን ተረት ተከትለን አይደለም፤ [17]ምክንያቱም ከግርማዊው ክብር "በእርሱ ደስ የሚለኝ የምወደው ልጄ ይህ ነው" የሚል ድምፅ በመጣለት ጊዜ ከእግዚአብሔር አብ ክብርና ሞገስ ተቀብሎአል፤ [18]እኛም ከእርሱ ጋር በቅዱሱ ተራራ ላይ በነበርንበት ጊዜ ይህ ድምፅ ከሰማይ ሲመጣ ሰምተናል።

[19]እንግዲያስ ትንቢታዊው ቃል ይበልጥ ተረጋግጦልናል፤ ሌሊቱ እስኪነጋና የንጋት ኮከብ በልባችሁ እስኪበራ ድረስ፣ በጨለማ ስፍራ ለሚበራ መብራት ጥንቃቄ እንደሚ ደረግ እናንተም ለዚህ ቃል ብትጠነቀቁ መልካም ታደርጋላችሁ። [20]ከሁሉ አስቀድሞ ይህን ልታውቁ ይገባችኋል፤ በመጽሐፍ ያለው የትንቢት ቃል ሁሉ ማንም ሰው በግሉ ራሱ መንገድ የሚተረጐመው አይደለም፤ [21]ምክንያቱም ትንቢት ከእግዚአብሔር የተላኩ ሰዎች በመንፈስ ቅዱስ ተመርተው ተናገሩት እንጂ ከቶ በሰው ፈቃድ የመጣ አይደለም።

1፥15 ሉቃ9፥31
1፥16 ማቴ17፥1-8፤ ማር13፥26፤14፥62
1፥17 ማቴ3፥17
1፥18 ማቴ17፥6
1፥19 መዝ119፥105፤ ሉቃ1፥78፤ 2ቆሮ4፥6፤1ጴጥ1፥10፤ራእ22፥16
1፥20 2ጴጥ3፥3
1፥21 2ሳሙ23፥2፤ ሐሥ1፥16፤3፥18፤ 2ጢሞ3፥16፤ 1ጴጥ1፥11
2፥1 ዘዳ13፥1-3፤ ኤር6፥13፤ ማቴ7፥15፤1ቆሮ6፥20፤1ጢሞ4፥1፤ይሁ4
2፥2 ይሁ4
2፥3 ቍ14፤ 2ቆሮ2፥17፤1ተሰ2፥5
2፥4 ዘፍ6፥1-4፤ 1ጢሞ3፥6፤ይሁ6፤ ራእ20፥1፡2

## ሐሰተኛ መምህራንና መጨረሻቸው

**2** ነገር ግን ሐሰተኞች ነቢያት በሕዝቡ መካከል እንደ ነበሩ እንዲሁም በእናንተ መካከል ሐሰተኞች መምህራን ይነሣሉ፤ እነ ርሱም የዋጃቸውን ጌታ እንኳ ክደው ጥፋት የሚያስከትል የስሕተት ትምህርት በስውር ያስገባሉ፤ በዚህም በራሳቸው ላይ ድንገተኛ ጥፋት ያመጣሉ። [2]ብዙዎች እስነዋሪ ድርጊ ቶቻቸውን ይከተላሉ፤ በእነርሱም ምክንያት የእውነት መንገድ ይሰደባል። [3]እነዚህ ሐሰተኞች መምህራን እየተስገበገቡ በፈጠራ ታሪካቸው ይበዘብዙዋችኋል። ፍርዳቸው ከጥንት ጀምሮ ዝግጁ ነው፤ መጥፊያቸውም አያንቀላፋም።

[4]እግዚአብሔር ኀጢአት የሠሩትን መላእክት ሳይራራላቸው ወደ ገሃነም[ሀ] ከጣላቸውና በጨለማ ጕድጓድ ውስጥ ለፍርድ ካስቀመጣቸው

”4 በግሪኩ *ታርታሩስ* ይለዋል

1፥15 *እነዚህን ነገሮች...ዘወትር ታስቡ ዘንድ፤* ጴጥሮስ እንዲያስተውሉ የፈለገው ዐቢይ ሐሳብ ሆን ብሎ ይሆን በአጋጣሚ፣ በማርቆስ ወንጌል ውስጥ ተጽፎ ይገኛል። ማርቆስ ወንጌሉን የጻፈው ከጴጥሮስ ባገኘው መረጃ እንደ ሆነ የክርስትና ትውፊት ይናገራል። የዚህ ትውፊት መሠረት ምናልባት ፣ የጴጥሮስ መልእክቶች ከማርቆስ ወንጌል አቀራረብ ጋር በጣም ስለ ሚቀራረቡ ሊሆን ይችላል።

1፥16 *ስለ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ...መምጣቱ፤* በደብረ ታቦር ላይ ክብሩን በገለጠ ጊዜ፣ ዳግም ሲመጣ በዘላለም መንግሥቱ የሚኖረውን ግርማና ክብር ደቀ መዛሙርቱ ከወዲሁ አይተዋል (ማቴ16፥28)። *የእርሱን ግርማ በዐይናችን ዐይተን፤* ይህ የሚያመለክተው ክርስቶስ በደብረ ታቦር ላይ በክብር የተገለጠበትን ሁኔታ ነው (ቍ17-18፤ ማቴ 16፥28-17፥8 ይመ)። *በ...ጥበብ የተፈጠረውን ተረት፤* ጴጥሮስ ለመልእክቱ መሠረት ያደረገው ፣በኢየሱስ አገልግሎት ያየው ልዕለ ተፈጥሮአዊ ክስተት ነው፤ እንደ መናፍቃን፣ በተፈጠሩት ተረታ ተረትና ልበ ወለድ ላይ የተመሠረተ አይደለም (2፥3ይመ)።

*1፥19-21፤* የጴጥሮስ መልእክት በሁለት ጠንካራ መሠረቶች ላይ የተመሠረተ ነው፤ (1) ጌታ በክብር በተሰወጠ ጊዜ ከእግዚአብሔር ዘንድ በመጣው ድምፅና (ቍ16-18) (2) እንዲሁም ዐቢይ ስፍራ ያለው የቅዱሳት መጻሕፍት ምስክርነት ነው (ቍ19-21)። ሌላው አማራጭ ደግሞ ጌታ በክብር ለመገለጡ ሐዋርያት ምስክር መሆናቸውና ቅዱሳት መጻሕፍት ስለዚህ ርእስ ጉዳይ የሚናገሩት ርግጥ መሆኑ ነው።

1፥19 *ይበልጥ ተረጋግጦልናል፤* ወይም "በጣም እርግጠኛ የሆነ" ማለት ነው።

*1፥20፤* ይህን ቍጥር በተመለከተ ፣ ሁለት ዐይነት አመለካከት አለ፤ (1) የትኛውም የትንቢት ቃል በግለሰብ ወይም በተናጠል አይተረጐምም (3፥16 ላይ ከተጠቀሱት የስሕተት አስተማሪዎች ጋር ያነጻጽሩ)። በአተረጓጐም ሂደት፣ መንፈስ ቅዱስ፣ መጽሐፍ ቅዱስና ቤተ ክርስቲያን በአንድነት መገኘት ይኖርባቸዋል። (2) ትንቢት፣ በነቢዩ አተረጓጐም ላይ ተመሥርቶ አልተጻፈም፤ ዐውደ ምንባቡም ይሄንን አመለካከት ያጠናክረዋል። ከቍ16-19 የተጠቀሰው፣ የሐዋርያት መልእክት ምንጭ ማን እንደ ሆነ ነው። ከሰው ሐሳብ የመነጨ ነው? ወይስ ከእግዚአብሔር? በቍ 21 ላይም የትንቢት ምንጭ ማን እንደሆነ ተገልጾአል። በመጽሐፍ ቅዱስ ከምናገኛቸው ትንቢቶች አንዱም በሰው አተረጓጐም ላይ ተመሥርቶ የመጣ አይደለም። በቍ20 ላይ ያለው ሐሳብ፣ "ምክንያቱም" ብሎ በሚጀምረው በቍ 21 ተጨማሪ ድጋፍ አግኝቶአል። ቍ21 የቍ 20 ሐሳብን እንደ ገና በማንሣት፣ እግዚአብሔርም የትንቢት ምንጭ መሆኑን በማስገንዘብ ያብራራል።

1፥21 *በመንፈስ ቅዱስ ተመርተው፤* የ2ጢሞ3፥16 ማብ ይመ። መጽሐፍ ቅዱስ ሲጻፍ የእግዚአብሔርም የሰውም ተሳትፎ ነበር። የቅዱሳት መጻሕፍት ትምህርት ምንጩ እግዚአብሔር በመሆኑ፣ መጽሐፍ ቅዱስ የሚናገረው ሁሉ እግዚአብሔር የተናገረው ነው። እንዲሁም ጸሐፊው እግዚአብሔር የተናገረውን መጻፍ ብቻ ሳይሆን፣ የራሱን መልእክት ሊያስተላልፍ ችሎአል። ሆኖም ግን ፣ የተላለፈው መልእክት ሁሉ ምንጩ እግዚአብሔር ነው፤ የሚመራውም መንፈስ ቅዱስ ነው።

2፥1 *ሐሰተኞች ነቢያት፤* 2ነገ18፥19፤ኢሳ9፥13-17፤ኤር 5፥31፤14፥14፤23፥30-32 ይመ። *በእናንተ መካከል ሐሰተኞች መምህራን ይነሣሉ፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ ያሉ ብዙ ምንባቦች፣ ስለ ነበሩትና ወደ ፊት ስለሚመጡት ሐሰተኞች መምህራን ያስጠነቅቃሉ (ማቴ24፥4-5፡11፤ሐሥ20፥29-30፤ሮሜ1፥6-9፤ፊል3፥2፤ ቈላ2፥4፡8፡18፡20-23፤ 2ተሰ2፥1-3፤1ጢሞ1፥3-7፡4፥1-3፤2ጢሞ3፥1-8፤1ዮሐ2፥18-19፡22-23፤2ዮሐ7-11፤ይሁ3-4ይመ)። *ጥፋት የሚያስከትል የስሕተት ትምህርት፤* በሰዎች መካከል መለያየትንና መከፋፈልን የሚያስከትል ወይም ትምህርቱን የተቀበሉትን ሰዎች ግብረ ገብና መንፈሳዊ ሕይወታቸውን የሚያበላሽ ነው። *የዋጃቸውን ጌታ፤* ሐሰተኞች መምህራን፣ አማኞች ነበሩ ማለት አይደለም፤ በእርግጥም ክርስቶስ ለእነርሱም ስለሞተ የኀጢአታቸው ዕዳ ተከፍሎአል፤ ሆኖም ግን ድነት ሊያገኙ የሚችሉት፣ ክርስቶስን አምነው ሲቀበሉት ብቻ ነው። (ይሁን እንጂ ሐሰተኞች መምህራን፣ አማኞች ነን ብለው ይናገሩ ነበር ቍ 20-23 ይመ)። *ድንገተኛ ጥፋት ያመጣሉ፤* በአካላቸው ላይ የሚደርሰው አደጋ ወይም ጕዳት ሳይሆን፣ ሲሞቱ ወይም ጌታ ዳግም ሲመጣ የሚደርስባቸው ድንገተኛ ፍርድንና ጥፋትን ያመለክታል (ከማቴ 24፥50-51፤ ከ2ተሰ 1፥9 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥2 *አስነዋሪ ድርጊቶቻቸውን፤* ልቅና፣ በግልጽ የሚፈጸም፣ ዕፍረት የሌለበት ድርጊት ነው። *የእውነት መንገድ፤* መዝ 119፥30 ይመ። ክርስትና እውነተኛ እምነት ብቻ ሳይሆን ትክክለኛ አኗኗርም ነው።

2፥3 *እየተስገበገቡ፤* ለገንዘብ ካላቸው ፍላጎት የተነሣ የክርስትናን እምነት ለግል ጥቅማቸው ሲሉ ይጠቀሙበታል። *ከጥንት ጀምሮ ዝግጁ ነው፤* ከብሉይ ኪዳን ዘመን ጀምሮ፣ ፍርድ ተወስኖባቸዋል (በክፉዎች ላይ ሲደርስ ስለነበው ጥፋት በምሳሌነት ከብሉይ ኪዳን የተጠቀሱትን ከቍ 4-9 ይመ)። *መጥፊያቸውም አያንቀላፋም፤* በመዘግየቱ የቀረ ቢመስልም በእነርሱ ላይ ጥፋት መድረሱ የማይቀር ነው።

*2፥4-8፤* እግዚአብሔር ጻድቃንን እንደሚታደግና ዐመፀኞችን እንደሚያጠፋ የተሰጡ ሦስት ምሳሌዎች ናቸው።

2፥4 *ኀጢአት የሠሩትን መላእክት፤* አንዳንዶች ይህ ኀጢአት በዘፍ 6፥2 ላይ የተጠቀሰውን እንደ ሆነ ይናገራሉ፤ ይህም የእግዚአብሔር ልጆች ከሰው ልጆች ሴቶች ጋር ተጋቡ የሚለውን መላእክት ከሰው ጋር ተጋቡ ማለት ነው ይላሉ፣ ከዚህ ዐይነት ግንኙነት የተገኙ ሰዎችም ኔፊሊም እንደሚባሉ ይናገራሉ (6፥4 እና የዘፍ 6፥2፡4 ማብ ይመ)። ይሁን እንጂ መላእክት ከሰው ልጆች ሴቶች ጋር ግብረ ሥጋ ፈጸሙ ማለት አስቸጋሪ ነው፤ በዚህ ቍጥር የተጠቀሰው ኀጢአት አጋንንት ሐዋን ከመውደቃቸው በፊት የተፈጸመ ሳይሆን አይቀርም። እነዚህ የወደቁ መላእክትም፣ ዲያብሎስና ርኵሳን መናፍስት ተብለው በአዲስ ኪዳን የተገለጹት ሳይሆኑ አይቀሩም። *ወደ ገሃነም ከጣላቸውና፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ግሪኮች እንጦርጦስ ይሉታል፤ ይህም እጅግ ክፉ የሆኑ መናፍስት ለቅጣት የሚወሰዱበት ቦታ ነው። አንዳንዶች የወደቁ መላእክት ሲታሰሩ፣ ሌሎቹ ደግሞ ሰይጣንን ለማገልገል አጋንንት ሆነው ለምን በነጻነት እንደ ተለቀቁ የሚያሳይ የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል የለም። *ለፍርድ፤* የመጨረሻውን ፍርድ የሚመለከት ሲሆን፣

[5]የጽድቅ ሰባኪ የነበረውንም ኖኅን ከሌሎች ሰባት ሰዎች ጋር አድኖ ለቀድሞው ዓለም ሳይራራ በኀጢአተኞች ላይ የጥፋት ውሃ ካመጣ፣ [6]ደግሞም ኀጢአት ለሚያደርጉ ሁሉ ምሳሌ እንዲሆኑ የሰዶምንና የገሞራን ከተሞች ዐመድ እስኪሆኑ ድረስ አቃጥሎ ከፈረደ ባቸው፣ [7]ጻድቅ የሆነውንና በዐመፀኞች ሴሰኛ ድርጊት እየተሣቀቀ የኖረውን ሎጥን ካዳነ፣ [8]ያ ጻድቅ ሰው በእነርሱ መካከል ሲኖር በሚያየውና በሚሰማው ነገር ነፍሱ ዕለት ዕለት በዐመፀኛ ድርጊታቸው ብትጨነቅም፣ [9]ጌታ፣ በእውነት እያመለኩት የሚኖሩትን ከፈተና እንዴት እንደሚያድናቸውና ዐመፀኞችን እየቀጣ ለፍርድ[^] ቀን እንዴት ጠብቆ እንደ ሚያቈያቸው ያውቃል። [10]በተለይም በርኩስ ምኞት የሥጋ ፍላጎታቸውን[^] የሚከተሉትንና ሥልጣንን የሚንቁትን ለፍርድ ጠብቆ ያቈያቸዋል ።

እነዚህ ሰዎች ደፋሮችና እብሪተኞች ስለ ሆኑ ሰማያውያንን ፍጡራን ሲሳደቡ አይፈሩም፤ [11]ነገር ግን መላእክት ከእነርሱ ይልቅ ብር ቱና ኀያል ሆነው ሳሉ፣ በጌታ ፊት በእነርሱ ላይ የስድብ ቃል አይሰነዝሩም። [12]እነዚህ ሰዎች ግን ምንም በማያውቁት ነገር እየገቡ ይሳደባሉ፤ እነርሱም ለመያዝና ለመገደል እንደ ተወለዱ፣ በስሜታቸው ብቻ እንደሚ መሩና ልቡናም እንደሌላቸው አራዊት ናቸው፤ የሚጠፉትም እንደ እንስሳት ነው።

[13]ስለ ዐመፃቸው የሚገባውን የዐመፅ ዋጋ ይቀበላሉ፤ በጠራራ ፀሐይ ሲፈነጥዙ እንደ ደስታ ይቈጥሩታል፤ በግብዣ ላይ ሳሉ ነውረ ኞችና ርኩሶች ሆነው ከእናንተም ጋር በፍቅር ግብዣ ላይ[−] ይቀመጣሉ፤ [14]ዐይናቸው ቅንዝር የተሞላ በመሆኑ ኀጢአትን ከመሥራት አይቈጠቡም፤ ጽኑ ያልሆኑትን ነፍሳት ያስታሉ፤ ስስትን የለመደ ልብ አላቸው፤ የተረገሙ ናቸው! [15]ቀናውን መንገድ ትተው፣ የዐመፅን ደመወዝ የወደደውን የቢዖርን ልጅ የበለዓምን መንገድ ተከትለው ስተዋል፤ [16]እርሱ ግን ስለ መተላለፉ ተገሥጾአል፤ መናገር የማ ይችል አህያ በሰው ቋንቋ ተናግሮ የነቢዩን እብደት ገታ። [17]እነዚህ ሰዎች የደረቁ ምንጮችና በዐውሎ ነፋስ የሚነዱ ደመናዎች ናቸው፤ የሚጠብቃቸውም ድቅድቅ ጨለማ ነው፤ [18]ከንቱ ቃል እየደረደሩ በስሕተት ከሚኖሩት መካከል አምልጠው የመጡትን

2፥5 ዘፍ6፥5-8፡ 19፤ዕብ11፥7፤ 1ጴጥ3፥20፤2ጴጥ3፥6
2፥6 ዘፍ19፥24፡25፤ ዘኍ26፥10፤ ማቴ10፥15፤11፥23፡24፤ሮሜ9፥29፤ይሁ7
2፥7 ዘፍ19፥16፤ 2ጴጥ3፥17
2፥8 ዕብ11፥4
2፥9 መዝ37፥33፤ ማቴ10፥15፤ ሮሜ15፥31፤ ራእ3፥10
2፥10 2ጴጥ3፥3፤ ይሁ8፡16፡18
2፥11 ይሁ9
2፥12 መዝ49፥12፤ ይሁ10
2፥13 ሮሜ13፥13፤ 1ቆሮ11፥20፡21፤ 1ተሰ5፥7፤ይሁ12
2፥14 ኍ3፡18፤ ኤፌ2፥3፤2ጴጥ3፥16 ያዕ1፥8
2፥15 ዘኍ22፥4-20፤ 31፥16፤ዘዳ23፥4፤ ይሁ11፤ራእ2፥14
2፥16 ዘኍ22፥21-30
2፥17 ይሁ12፡13
2፥18 ኍ20፤ 2ጴጥ1፥4፤ይሁ16

[^] 9 ወይም ዐመፀኞችን ለቅጣት እስከ ፍርድ ቀን ድረስ
[^] 10 ወይም የኀጢአተኛ ባሕርያቸውን
[−] 13 በአንዳንድ ቅጆች በፍቅር ግብዣቸው ላይ የሚል የለም

ምናልባት በራእ 20፥11-15 ላይ የተጠቀሰው የታላቁን ነጭ ዙፋን ፍርድ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል።

2፥5 *የጽድቅ ሰባኪ የነበረውንም፤* ስለ ኖኅ ይህን የመሰለ አባባል በየትኛውም የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል ውስጥ አይገኝም። የሲፍ ወልደ ክርዮንና (እንቲኩዊት) በ3፡1፡1ኛ ቀለሜንጦስ (7፡6፤9፡4 ) ስለ ቀን ተመሳሳይ አባባል አላቸው። *ከሌሎች ሰባት ሰዎች፤* የኖኅ ሚስት፣ ሦስቱ ወንዶች ልጆቹና ሦስቱ ምራቶቹ (የልጆቹ ሚስቶች) ሲሆን፣ በምንተኛው ኖኅ ነበር፤ (1ጴጥ 3፥20 ይመ)። *በኀጢአተኞች፤* ዘፍ6፥5፡11-12 ይመ።

2፥6 *የሰዶምና የገሞራን ከተሞች…ከፈረደባቸው፤* ዘፍ 19 ይመ።

2፥7 *በዐመፀኞች…ድርጊት እየተሣቀቀ፤* ዘፍ 19፥4-9 ሎጥ ምን ያህል እንደ ተጨነቀና "ጻድቅ ሰው" ተብሎ እየተጠራ፣ ሴቶች ልጆቹን በግብረ ሥጋ እንዲያስነውሩአቸው በሰዶም ለሚ ኖሩ ርኩሳን ሰዎች አሳልፎ መስጠቱ ግራ የሚያጋባ ነው፤ ይሁን እንጂ እርሱን ብለው የመጡትን እንግዶች ክብር ለማስጠበቅ መከራረፉ እንደ መልካም ምግባር ተቈጥሮለታል (የዘፍ19፥8 ማብ ይመ )።

*2፥9፤* ጴጥሮስ በቍ 4-8 ላይ የገለጸውን በማጠቃለል፣ የክፉዎች መምጣት ቅጣትን እንደሚያስከትል ከወዲሁ ይናገራል።

2፥10 *በተለይም፤* በጴጥሮስ ዘመን የነበሩ መናፍቃን ወደ ፍርድ መምጣታቸው በሁለት ምክንያቶች ርግጥ ነው፤ (1) በኀጢ አት የረከሰ ምኞታቸውን ተከትለው ስለሚኖሩና፣ ምናልባትም የሰዶማውያን ኀጢአት የሆነውን ግብረ ሰዶም ስለሚፈጽሙ (ዘፍ 19፥5 ይመ)፤ (2)ባለ ሥልጣናትን ስለሚንቁ ነው። *በማያውያንን ፍጡ ራን ሲሳደቡ፤* ሥልጣን ያላቸውን ለመናቃቸው ጥሩ ምሳሌ ነው። ከዚህም የተነሣ፣ ምድራዊ ባለ ሥልጣናትን፣ የቤተ ክርስቲያን መሪዎችን መናቅ የእነዚህ ሰዎች ወራዳ ባሕርያት ናቸው። ከዚህ በተጨማሪም፣ መላእክትን መሳደብም መለያ ባሕርያቸው ነው፣ በይሁ 8-10 ላይ ያለው ተጓዳኝ ምንባብ የሚናገረው ስለ መላእክት በመሆኑ፣ ይኸኛውን አመለካከት ያጠናክራል።

2፥11 *መላእክት…የስድብ ቃል አይሰነዝሩም፤* ኀያላን የሆኑ ቅዱሳን መላእክት እንኳ፣ ከእነርሱ በታች ከሆኑት የወደቁ የክፉት መላእክት ይልቅ ብርቱ ሲሆኑም፣ ክፉ ቃል አይናገሯቸውም።

2፥12 *በማያውቁት ነገር፤* ምናልባት ጴጥሮስ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ትምህርት በለጋነት ደረጃ የነበረውንና በሁለተኛው ምእተ ዓመት ጎልቶ የወጣውን የኖስቲሲዝም የስሕተት ትምህርት ሲሆን ይችላል (በ1ዮሐንስ መግቢያ ላይ ኖስቲሲዝም የሚለውን ይመ)፤ የዚህ ትምህርት አራማጆች ልዩ ምስጢራዊ ዕውቀት እንዳላቸው ይናገሩ ነበር። እንግዲህ እነዚህ ልዩ እውቀት አለን ባዮች በክፉ የድንቍርና ሕይወት መኖራቸው ምፀታዊና፣ የኑሮአቸው ውጤ ትም ድፍረት የተሞላበት ስድብና የመሰከትን ነገር ማቃለል ነበር። *አራዊት፤* ማመዛዘል የሌለበት ውጣት ነው። አእምሮ እንደሌላቸው እንስሳትና እንደሚታረዱ ከብቶች ናቸው፤ ዕድል ፈንታቸው ጥፋት ነው።

2፥13 በጠራራ ፀሐይ ሲፈነጥዙ፤ 1ተሰ5፥7 ይመ። አረ ማውያን እንኳ፣ ጨለማን ተገን በማድረግ እኩይ ተግባራቸውን ያራምዳሉ፤ እነዚህ መናፍቃን ግን ዕፍረተ ቢስ ናቸው። *በግብዣ ላይ ሳሉ፤* በአማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ይህ ሐሳብ በይሁ 12 ላይ "የፍቅር ግብዣ" ከሚለው ጋር ይመሳሰላል፤ እነዚህ ሐሰተኞች መምህራን፣ የጥንት አብያተ ክርስቲያናት ከጌታ ራት በኋላ አብረው በሚሳተፉት "የፍቅር ግብዣ" ላይ ይገኙ እንደ ነበር ይጠቁማሉ በዚህ በተቀደሰው ሥርዐት ላይ እየተገኙ፣ ዐመላቸው የሆነውን መዳራት እሸልከው ያስገቡና ይሉኝታ የሌለውን ድርጊ ታቸውን ያሠረጉ ይመስላል።

2፥14 *ዐይናቸው ቅንዝር የተሞላ፤* ያዩአትን ሴት ሁሉ በፍትወት ዐይን የሚመለከቱና የግብረ ሥጋ ፍላጎታቸው ማርኪያ ለማድረግ የሚቋምጡ ማለት ነው። *ኀጢአትን ከመሥራት አይቈጠቡም፤* ዐይናቸው በምኞት የተሞላ ነው። *ጽኑ ያልሆኑትን.. ያስታሉ፤* በግሪኩ "ማሳት" የሚለው ቃል በተመሳሳይ ጥቅም ላይ የዋለበት ያዕ1፥14 ላይ ይመ፤ ቃሉ ዓሣ አጥማጅ በመንጠቆ ጫፍ ላይ ምግብ በማስቀመጥ ዓሣን እንዴት እንደሚያጠምድ ያመለ ክታል። *ስስትን የለመደ፤* በግሪኩ እንደ ስፖርተኛ ልምምድ እንደሚያደርጉ ያመለክታል፤ ይህም የአካል ብቃት ልምምድ ሳይሆን የስግብግብነት ነው።

2፥15 *የቢዖርን ልጅ የበለዓምን መንገድ፤* ዘኍ22-24 ይመ። እግዚአብሔር ሲከለክለውም እንኳ፣ በለዓም እስራኤልን ለመረገም ተዘጋጅቶ ነበር። ባላቅ ለሰጠው ቃል የገባለትን ገንዘብ ለማግኘት ጓጓ። በተመሳሳይ ሁኔታ እነዚህ ሐሰተኛ መምህራን ከየዋሃን አድ ማጮቻቸው ገንዘብ ለመሰብሰብ ባላቸው ፍላጎት ምክንያት በደለኞች መሆናቸው ግልጽ ነው። አህያ የነቢዩን እብደት መገሠጹ የበለዓምን ብቻ ሳይሆን፣ በጴጥሮስ ዘመን የነበሩትን የሐሰተኛ መምህራን ጅልነት የሚያሳይ ነው።

2፥17 *የደረቁ ምንጮች፤* የክፉ መታለልን የሚያሳይ ሥዕላዊ አገላለጽ ነው። ውሃ የተጠማ መንገደኛ ቀዝቃዛ ውሃ ፈልጎ ጥማቱን ለማርካት ወደ ምንጭ እንደሚሄድና ደረቅ ሆኖ እንደሚያገኘው ማለት ነው። ሐሰተኛ መምህራንም እንደዚሁ የሚያረካ እውነት የሚገኝባቸው ይመስላሉ፤ በተግባር ሲታይ ግን የሚቀርቡት አንዳች ነገር የላቸውም። *በዐውሎ ነፋስ የሚነዱ ደመናዎች* ካፊያ ሳይጥሉ የሚበተኑ ናቸው። *ድቅድቅ ጨለማ፤* የመጨረሻ ዕጣቸው ሲኦል ነው።

2፥18 *ከንቱ ቃል እየደረደሩ፤* ለአዲስ እማኝ እውነት የሚመስል ቃል ይናገራሉ፤ ነገር ግን የሚናገሩት ከንቱ ነው።

ስዎች በሴስኛ ሥጋዊ ምኞት በማባበል ያታልላሉና። [19]እነርሱ ራሳቸው የጥፋት ባሪያዎች ሆነው ሳሉ፣ ሌሎችን ነጻ ትወጣላችሁ እያሉ ተስፋ ይሰጧቸዋል፤ ሰው ለተገዛለት ለዚያ ነገር ባሪያ ነውና። [20]ጌታችንንና አዳኛችንን ኢየሱስ ክርስቶስን በማወቅ ከዓለም ርኵሰት ካመለጡ በኋላ እንደ ገና ተጠላልፈው ቢሸነፉ ከመጀመሪያው ይልቅ የኋለኛው ሁኔታቸው የከፋ ይሆንባቸዋል። [21]የጽድቅን መንገድ ካወቁ በኋላ ከተሰጣቸው ቅዱስ ትእዛዝ ወደ ኋላ ከሚመለሱ፣ ቀድሞውኑ የጽድቅን መንገድ ባላወቁዋት ይሻላቸው ነበር። [22]“ውሻ ወደ ትፋቱ ይመለሳል” እንዲሁም “ዐሣማ ቢታጠብም ተመልሶ በጭቃ ላይ ይንከባለላል” የሚለው ምሳሌ እውን ይሆንባቸዋል።

## የጌታ ቀን

**3** ወዳጆች ሆይ፤ ይህ አሁን የምጽፍላችሁ ሁለተኛው መልእክት ነው። ሁለቱንም መልእክቶች የጻፍሁላችሁ ቅን ልቦናችሁን እንድታነቃቁ ለማሳሰብ ነው፤ [2]ደግሞም ቀድሞ በቅዱሳን ነቢያት የተነገረውን ቃል እንዲሁም በሐዋርያታችሁ አማካይነት በጌታችንና በአዳኛችን የተሰጠውን ትእዛዝ እንድታስቡ ነው።

[3]ከሁሉ አስቀድሞ ይህን ዕወቁ፤ በመጨረሻው ዘመን የራሳቸውን ክፉ ምኞት የሚከተሉ ዘባቾች እየዘበቱ ይመጣሉ። [4]እነርሱም፣ “ ‘እመጣለሁ’ ያለው ታዲያ የት አለ? አባቶች ከሞቱበት ከፍጥረት መጀመሪያ እንሥቶ እስካሁን ድረስ ሁሉም ነገር እንዳለ ይኖራል” ይላሉ። [5]ነገር ግን እነዚህ ሰዎች ሰማያት ከጥንት ጀምሮ በእግዚአብሔር ቃል ተፈጥረው እንደሚኖሩ፣ መሬትም በውሃ መካከልና በውሃም እንደ ተሠራች ሆን ብለው ይክዳሉ፤ [6]በዚያን ጊዜ የነበረው ዓለም በውሃ ተጥለቅልቆ ጠፋ። [7]በዚያው ቃል ደግሞ አሁን ያሉት ሰማያትና ምድር፣ ኀጢአተኞች እስከሚጠፉበት እስከ ፍርድ ቀን ድረስ ለእሳት ተጠብቀዋል።

2፥19 ሮሜ6፥16
2፥20 ማቴ12፥45፤ 2ጴጥ1፥2፡11፤3፥18
2፥21 ሕዝ18፥24፤ ዕብ6፥4-6፤ 10፥26፡27
2፥22 ምሳ26፥11
3፥1 1ቆሮ10፥14፤ 2ጴጥ1፥13
3፥2 ሉቃ1፥70፤ ሐሥ3፥21፤ኤፌ4፥11
3፥3 1ጢሞ4፥1፤ 2ጢሞ3፥1፤ 2ጴጥ2፥10፤ይሁ18
3፥4 ኢሳ5፥19፤ ሕዝ12፥22፤ ማቴ24፥48፤ ማር10፥6፤ ሉቃ17፥30
3፥5 ዘፍ1፥6፡9፤ መዝ24፥2፤ዕብ11፥3
3፥6 ዘፍ7፥21፡22፤ 2ጴጥ2፥5
3፥7 ቍ10፡12፤

---

*በማባበል ያታልላሉና፣* የቍ 14 ማብ ይመ (“ያሲታሉ”)። *አምልጠው የመጡትን ሰዎች፣* አረማውያን ከሆኑ ባልንጀሮቻቸው ተለይተው የመጡትን አዲስ አማኞችን ማለት ነው። እነዚህ ከንቱ የሆኑ ሐሰተኛ መምህራን በመንፈሳዊ ሕይወት ለማደግ ገና ዕድል ያላገኙ አዲስ አማኞችን ያጠምዳሉ።

2፥19 *ነጻ ትወጣላችሁ እያሉ ተስፋ ይሰጧቸዋል፣* ከግብረ ገብ ገዴታ ነጻ መሆንን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ከ1ቆሮ6፥12-13፤ገላ5፥13 ጋር ያነጻጽሩ)። ከሕግና ከሥርዐት ነጻ ትወጣላችሁ የሚሉ እነዚህ ሰዎች፣ ራሳቸው በጥፋት ባርነት የታሰሩ ናቸው። ከሕግ ተገዥነት ነጻ ነኝ ማለት የኀጢአት ባሪያ መሆንን ያመለክታል፤ ይህ ዐይነት ነጻነት እንደ ልብ ወደ መሆን ያመራል ማለት ነው ።

*2፥20-22፣* አንዳንድ ሰዎች ይህ ክፍል የዳነ አማኝ ድነቱን ሊያጣ እንደሚችል የሚያሳይ ግልጽ ማስረጃ ነው ይላሉ። አማኙ ጌታን ያውቃል፤ ከዓለም ጥፋት አምልጦአል፤ የጽድቅንም መንገድ ያውቃል፤ ከእግዚአብሔር ቃል መልእክት ተመልሶ የጥንቱን የአኗኗር ልማድ ይከተላል፤ ዕውቀቱም ሆነ የሕይወት ለውጥ ማግኘቱ እውነተኛ ነበር፤ ወደ ጥንቱ የአኗኗር ልማድ መመለሱ እውን ነበር ይላሉ። ሌሎች ደግሞ ድነቱን ዐጣ የተባለው ሰው፣ እግዚአብሔርን ማወቁንና የጽድቅን መንገድ መከተሉ ቀድሞውንም ቢሆን እውነተኛ አልነበረም፤ በእውነት ዳግም ከተወለደ፣ በእምነቱ እስከ መጨረሻው ይጸናል ይላሉ።

2፥20 *ከዓለም ርኵሰት ካመለጡ በኋላ፣* ቀድሞ ለክርስቶስ ያምኑ የነበሩትን ሐሰተኛ መምህራንን የሚመለከት ነው። ክርስቶስን ዐውቀናል በማለታቸው የሕይወት ለውጥ ታይቶባቸው ሊሆን ይችላል። ካመለጡ በኋላ የሚለው ሐረግ ግን የተለወጡ ምእመናን እንደ ሆኑ የሚያሳይ ይመስላል። *እንደ ገና ተጠላልፈው ቢሸነፉ፣* ፍጹም ወደ ቀድሞው የኀጢአት ሕይወት መመለስን የሚያመለክት ነው።

2፥21 *ቅዱስ ትእዛዝ፣* ሰዎች ሁሉ እንዲቀበሉ የታዘዙትን ሙሉ የክርስትና መልእክት ነው። *የጽድቅን መንገድ ባላወቁዋት ይሻላቸው ነበር፣* ይህን መንገድ ማወቅ ኀላፊነትን ይጨምራል፤ እውነትንም ረግጦ መሄድ ልብን ያደነድናል። ክርስትና ገና ከጅምሩ “መንገድ” ተብሉ ይታወቅ ነበር (ሐሥ 9፥2፤18፥25፤19፥9፡23፤22፥4፤ 24፥14፡ 22)።

2፥22 *ውሻ...ይመለሳል፣ ዐሣማ....ተመልሶ...፣* በሁለቱም ሁኔታ የእንስሳቱ ባሕርይ አልተለወጠም። ዐሣማ ወደ ጭቃ የሚመለሰው ተፈጥሮው ያው ዐሣማ በመሆኑ ነው። ስለዚህ ለውጡ ውጫዊ መተታጠብ ብቻ ነበር ማለት ይቻላል።

3፥1 *ወዳጆች ሆይ፣* ቍ8፡14፡17፤1ጴጥ2፥11፤4፥12ይመ። *ሁለተኛው መልእክት፣* የመጀመሪያው መልእክት አንደኛ ጴጥሮስ ሊሆን ይችላል፤ ይሁን እንጂ ደፍሮ ለመናገር የሚያስቸግር ነገር አለ፤ ለምሳሌ 1ኛ ጴጥሮስን በእርግጥነት እንደ ማሳሰቢያ መልእክት መወሰድ እጅግ አዳጋች ነው። *ለማሳሰብ፣* 1፥12-13፡15 ይመ።

3፥2 *በቅዱሳን ነቢያት፣* በብሉይ ኪዳን ያሉት ማለት ነው። *በሐዋርያታችሁ፣* ጴጥሮስ የብሉይ ኪዳን ነቢያትንና የአዲስ ኪዳን ሐዋርያትን በእኩል ደረጃ ላይ ያስቀምጣቸዋል። ሁለቱም ለእግዚአብሔር ቅዱስ እውነት መተላለፊያ መሣሪያ ነበሩ። ከሐዋርያት መካከል አንዱ የሆነው ጴጥሮስ፣ ሐዋርያትን በመወከል በዕውቀትና በሥልጣን ለመናገር ይችላል። *ትእዛዝ፣* የ2፥21 ማብ ይመ።

3፥3 *ከሁሉ አስቀድሞ፣* በ1፥20 ላይ የሚገኘው ይኸው አባባል፣ በጣም አስፈላጊ ለሆነው ነገር ትኵረት መስጠትን በሚያሳይ መልኩ አገልግሎት ላይ ውሎአል። *በመጨረሻው ዘመን* ክርስቶስ መጀመሪያ ከመጣበት ጊዜ ጀምሮ ያለውን ዘመን የሚያመለክት አባባል ነው። የመጀመሪያውና የዝግጅት ዘመን ከሆነው ከብሉይ ኪዳን ዘመን ጋር ሲነጻጸር ይህ የመጨረሻው ነው። ስለዚህ የክርስትና ዘመን የብሉይ ኪዳን ትንቢት መፈጸም የጀመረበት ጊዜ ነው። *ዘባቾች...ይመጣሉ፣* በም 2 ላይ የተገለጹት ሐሰተኞች መምህራን ሊሆኑ ይችላሉ (ለምሳሌ፤ ክፉ ምኞታቸውን ይከተላሉ ፤ ከ2፥10፡18-19 ጋር ያነጻጽሩ)። በምዕራፍ 3 ላይ ግን በአጽንዖት የተጠቀሰው የክርስቶስ ዳግም ምጽአት ነው። ምናልባት እነዚህ ሰዎች ፍርድም ሆነ የግብረ ገብ ኀላፊነት የለብንም ይሉ የነበሩ ቀደምት የኖስቲክ ትምህርት አራማጆች ሳይሆኑ አይቀሩም።

3፥4 *‘እመጣለሁ’ያለው፣* ክርስቶስ ነው። *አባቶቻችን ከሞቱበት ... መጀመሪያ እንሥቶ፣* ከክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ በኋላ የሞቱትን የመጀመሪያዎቹን ክርስቲያኖች (ለምሳሌ፡ እስጢፋኖስ፣ የዮሐንስ ወንድም ያዕቆብ እንዲሁም ሌሎች የቤተ ክርስቲያን መሪዎች ማለት ነው፤ ከዕብ13፥7 ጋር ያነጻጽሩ) ወይም ርእሳን አበውን ሊሆን ይችላል። *ሁሉም ነገር እንዳለ ይኖራል፣* ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት ያላቸው አሉታዊ አመለካከት፣ ክርስቶስ እስከ አሁን ስላልመጣ ወደ ፊትም አይመጣም የሚል ነበር። እነዚህ ሰዎች ከዕለታዊ ኑሮአችን እንደምንመለከተው፤ ፍጥረት በአምላክ ጣልቃ ገብነት አትገዛም ባዮች ናቸው፤ ለዚህም የሚቀርቡት ማስረጃ፡ (1) አባቶች ከሞቱበት ከ30 ዓመት ወዲህ (2)እንዲሁም ከፍጥረት መጀመሪያ እንሥቶ ይህ አልሆነም ባዮች ናቸው።

3፥5 *በእግዚአብሔር ቃል፣* እግዚአብሔር “ብርሃን ይሁን” (ዘፍ1፥3) ብሎ እንዳዘዘው ዐይነት ማለት ነው። *መሬትም ውሃ መካከልና በውሃም እንደ ተሠራች፣* በዘፍ1፥6-10 ይመ፤ በየብስ ላይ የነበረው ውሃ በንዋ ላይ ካለው ውሃ እንዴት እንደ ተለየ፣ ተራሮችም እንዴት እንደተገለጡና በየብስ ላይ የነበረው ውሃ እንዴት ወደ ውቅያኖሶች እንደ ተሰበሰበ ይመ። *ሆን ብለው ይክዳሉ፣* በኖኅ ዘመን የነበረው የጥፋት ውሃ፣ አምላክ በፈጠረው ዓለም ውስጥ ጣልቃ መግባቱን የሚያሳይ መሆኑን ሳያውቁ ቀርተው ሳይሆን፣ ሆን ብለው የፈጸሙት ክሕደት ነው። የመከራከሪያ ነጥባቸው ስሕተት ሊቀብሉ አይፈልጉም።

3፥6 *ዓለም በውሃ ተጥለቅልቆ ጠፋ፣* ጴጥሮስ፣ የዘባቾቹ የመከራከሪያ ነጥብ ስሕተት መሆኑን ያመለክታል። ከፍጥረት ጊዜ ጀምሮ እግዚአብሔር ዓለም በምትመራበት ሕግ ውስጥ ጣልቃ በመግባት ክንዱን አሳይቶአል፤ ለዚህም ማስረጃ አንዱ የጥፋት ውሃ ነው። “ዓለም” የሚለው ቃል ምድርን ወይም በምድር የሚኖሩትን ሰዎች የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ከዮሐ 3፥16 ጋር ያነጻጽሩ)። ከኖኅና ከቤተሰቡ በስተቀር ሰዎች ሁሉ በጥፋት ውሃ ጠፍተዋል።

3፥7 *በዚያው ቃል፣* ዓለምን የፈጠረውና (ቍ5) በኖኅ ዘመን በነበሩ ኃጥአን ላይ የጥፋት ውሃ ያመጣው የእግዚአብሔር

[8]ወዳጆች ሆይ፤ በጌታ ዘንድ አንድ ቀን እንደ ሺህ ዓመት፣ ሺህ ዓመትም እንደ አንድ ቀን መሆኑን ይህን አንድ ነገር አትርሱ። [9]አንዳንድ ሰዎች የዘገየ እንደሚመስላቸው የተስፋ ጌታ ቃሉን ለመፈጸም አይዘገይም፤ ነገር ግን ማንም እንዳይጠፋ፣ ሁሉ ለንስሓ እንዲበቃ ስለ እናንተ ይታገሣል።

[10]የጌታ ቀን ግን እንደ ሌባ ይመጣል፤ በዚያች ቀን ሰማያት በታላቅ ድምፅ ያልፋሉ፤ የሰማይም ፍጥረት በእሳት ይጠፋል፤ ምድርና በእርሷም ላይ ያለ ነገር ሁሉ ይቃጠላል።

[11]እንግዲህ ሁሉም ነገር በዚህ ሁኔታ የሚጠፋ ከሆነ፣ እናንተ እንዴት ዐይነት ሰዎች ልትሆኑ ይገባችኋል? አዎን፣ በቅድስናና በእውነተኛ መንፈሳዊነት ልትኖሩ ይገባችኋል፤ [12]ደግሞም የእግዚአብሔርን ቀን እየተጠባበቃችሁ መምጫውን ልታፋጥኑ ይገባል። በዚያን ቀን ሰማያት በእሳት ተቃጥለው ይጠፋሉ፤ የሰማይም ፍጥረት በታላቅ ትኩሳት ይቀልጣል። [13]እኛ ግን ጽድቅ የሚኖርበትን አዲስ ሰማይና አዲስ ምድር በተስፋ ቃሉ መሠረት እንጠባበቃለን።

[14]ስለዚህ ወዳጆች ሆይ፤ እነዚህን ሁሉ ነገሮች የምትጠባበቁ ስለ ሆናችሁ፣ ያለ ነውርና ያለ ነቀፋ ከእርሱ ጋር በሰላም እንድትገኙ ትጉ። [15]የጌታችን ትዕግሥት እናንተ እንድትድኑ እንደ ሆነ አስቡ፤ እንዲሁም ወንድማችን ጳውሎስ እንደ ተሰጠው ጥበብ መጠን ጻፈላችሁ፤ [16]እርሱ ስለ እነዚህ ነገሮች በመልእክቶቹ ሁሉ ጽፎአል፤ በመልእክቶቹም ውስጥ በቀላሉ ለመረዳት የሚያዳግቱ ነገሮች አሉ። ዕውቀት የጐደላቸውና ጽናት የሌላቸው ሰዎች ሌሎችን ቅዱሳት መጻሕፍት እንደሚያጣምሙ፣ እነዚህንም ደግሞ ለገዛ ጥፋታቸው ያጣምማሉ።

[17]እንግዲህ ወዳጆች ሆይ፤ ይህን አስቀድማችሁ ስላወቃችሁ፣ ጸንታችሁ ከቆማችሁበት መሠረት በዐመፀኞች ስሕተት ተስባችሁ እንዳትወድቁ ተጠንቀቁ።

ማቴ10፥15፤2ተሰ1፥7
3፥8 መዝ90፥4
3፥9 ዕን2፥3፤ ሮሜ2፥4፤ 1ጢ2፥4፤ ዕብ10፥37፤ራእ2፥21
3፥10 ቍ7፡12፤ ኢሳ34፥4፤ ማቴ24፥35፤ ሉቃ12፥39፤2ተሰ1፥7 ፤ራእ21፥1
3፥12 ቍ10፤ መዝ50፥3፤1ቆሮ1፥7
3፥13 ኢሳ65፥17፤ 66፥22፤ራእ21፥1
3፥14 1ተሰ3፥13
3፥15 ቍ9፤ ሮሜ2፥4፤ኤፌ3፥3
3፥16 ቍ2፤ መዝ56፥5፤ኤር23፥36፤ ያዕ1፥8፤ 2ጴጥ2፥14
3፥17 1ቆሮ10፥12፤ 2ጴጥ2፥7፡18፤ ራእ2፥5

10 በአንዳንድ ቅጆዎች *ምድር ወና ትሆናለች ይላል*
12 *ወይም የእግዚአብሔርን ቀን መምጣት በናፍቆት ስትጠብቁ*

ቃል፣ ሰዛሬውም ዓለምና ሰኃጥአን ላይ የጥፋት እሳት ያመጣል።

3፥8 *ሺህ ዓመትም እንደ አንድ ቀን፤* ከመዝ 90፥4 ጋር ያነጻጽሩ። እግዚአብሔር ጊዜን የሚመለከተው ሰዎች በሚያዩበት መንገድ አይደለም። እርሱ በጊዜ የማይለካ ዘላለማዊ ስለ ሆነ ጊዜን የሚመለከተው ስዘላለማዊነቱ ዕይታ ነው፤ በመሆኑም ዘመናት እንደ አንድ ቀን ፣ አንዲቷ ቀንም ከረጅሙ ዘመን እጥራ አትታየውም። ለእግዚአብሔር ዘንድ ጊዜ አንጻራዊ በመሆኑ ሰዎች ትዕግሥት አጥተው ሲጨነቁ፣ እርሱ ሁሉን በትዕግሥት ይመለከታል።

*3፥9፤* እግዚአብሔር የዓለምን ታሪክ ወደ ፍጻሜ ከማምጣት የዘገየ ቢመስልም፣ ከግዴለሽነት የተነሣ ሳይሆን፣ ሰዎች ወደ ንስሓ እንዲደርሱ ከመታገሡ የተነሣ ነው። ስለዚህ እነዚህ ዘባቾች በሁለት ነጥብ ተሳስተዋል፤ ይኸውም (1) ከተፈጠረ ጀምሮ እግዚአብሔር የፈጠረውን ዓለም ለፍጥረት ሕጋጋት ብቻ ትቶታል፤ ጣልቃ ገብቶ ለእጁ ነክቶት እያውቅም ማለታቸው ነው (የጥፋት ውሃ እግዚአብሔር ለፈጠረው ዓለም ሥርዐት ውስጥ ጣልቃ እንደገባ የሚያሳይ ነው፤ ቍ4-6) (2) እግዚአብሔር የዘገየ የመሰለበትን ምክንያት በውል አልተረዱትም (እግዚአብሔር የትዕግሥት እምላክ ነው)።

3፥10 *የጌታ ቀን፤* የኢሳ2፥11፡17፡ 20፤ አሞ5፥18፤1ተሰ5፥2 ማብ ይመ። *እንደ ሌባ፤* ሳይታሰብ እንዲሁም ለድንገት ማለት ነው። *ሰማያት በታላቅ ድምፅ ያልፋሉ፤* እንደ ትንቢተ ዳንኤልና እንደ የሐንስ ራእይ ባሉ መጻሕፍት ውስጥ የተለመደ የአቡቀለምሲሳዊን አገላለጽ ነው። የመጨረሻውን ዘመን በተመለከተ አቡቀለምሲሳዊን ጽሑፎች ሥዕላዊ ገለጻን፣ ቃል በቃል መተርጐም የለበትም፤ ምክንያቱም ጸሐፊያኑ ለመግለጽ አስቸጋሪ የሆነውን ሐሳብ ለተደራሲያኑ በሚገባ መንገድ ለማስተላለፍ የተጠቀሙበት መንገድ በመሆኑ ነው። ልክ እንደዚሁ በመጀመሪያው መቶ ክፍለ ዘመን የነበረ ጸሓፊ፣ በአቶሚክ ዘመን ያለውን የአሁኑን ዘመን ሰው ሐሳብ ለመግለጽ እንደሚያስቸግረው ማለት ነው። በዚህ ክፍል ለመግለጽ የተሞከረው ሰማያት በሚጠፉበት ጊዜ የሚሰማውን ኀይለኛ ድምፅ ነው (ቍ12 ይመ)። *በእሳት፤* ቍ7፡12 ይመ። *ምድር...ይቃጠላል፤* እማራጭ ትርጕሙን ይመ። ለምድር ያሉ ሁሉ ይጠፋሉ፤ ወይም ምድርና የሰዎች ሥራ ሁሉ፣ ለእግዚአብሔር የፍርድ ወንበር ፊት ይቀርባሉ ማለት ነው። *በእርሷም ላይ ያለ ነገር* ምናልባት ይህ ሰማያዊ አካላትን ወይም የቍሳዊውን ፍጥረት ንጥረ ነገሮች ያመለክታል፤ እነዚህም ንጥረ ነገሮች ለመጀመሪያ መቶ ክፍለ ዘመን መሬት፣ አየር፣ እሳትና ውሃ እንደ ሆኑ ይታመናል፣ ለዘመናችን ያለው ሳይንስ ግን ሀይድሮጂን፣ አክሲጂን፣ ካርቦንና ወዘተ ይላቸዋል።

3፥11 *ሁሉም ነገር...የሚጠፋ ከሆነ፤* ቍሳዊው ዓለም የሚለወጥ ወይም የሚጠፋ ከሆነ ለሰዎች የሚዛን ፋይዳና ቀዳማዊ ትኩረት ላይ ለውጥ ማምጣቱ አይቀሬ ነው። የዚህም ውጤት ለቅድስና መኖር (ከኀጢአት መለየት ለእግዚአብሔር መኖር ማለት ነው)፣ እግዚአብሔርንም መምሰል ነው (እግዚአብሔርን ለማምለክ መትጋት ማለት ነው)። ማቴ25፥13፤1ተሰ5፥6፡8፡11፤ 2ጴጥ1፥13-16 ጋር ያነጻጽሩ።

3፥12 *የእግዚአብሔርን ቀን፤* "የጌታ ቀን" ከሚለው ጋር ይመሳሰላል (ቍ10)፤ ምክንያቱም ሁለቱም ሐረጎች ተመሳሳይ ነገሮችን ያመለክታሉ (ከራእ16፥14 ጋር ያነጻጽሩ)። *መምጫውን ልታፋጥኑ፤* የእግዚአብሔር ሕዝብ የእግዚአብሔርን ዐላማ ከግብ ለማድረስ ጠንክሮ ቢሠራ የቀኑን መምጣት ሊያፋጥነው ይችላል። እግዚአብሔር ሰዎች ንስሓ ገብተው ወደ እርሱ እንዲመለሱ ስለሚፈልግ (ቍ9)፣ ክርስቲያኖች የምሥራቹን ቃል ለሌሎች በማዳረስ ሰዎችን ወደ ክርስቶስ ቢያመጡ ምጽአቱ በቶሎ ይሆናል (ከሐሥ3፥19-20 ጋር ያነጻጽሩ)። የቅድስና ሕይወት (ቍ11) የክርስቶስን ምጽአት እንደሚያፋጥነው ሁሉ፣ ጸሎትም እንዲሁ ነው (ማቴ6፥10)፤ *ሰማያት...ይጠፋሉ፤* ቍ10 ይመ። *ፍጥረት በታላቅ ትኩሳት ይቀልጣል፤* ቍ 10፤ ኢሳ34፥4 ይመ።

3፥13 *ጽድቅ የሚኖርበትን፤* ጻድቅ በዚያ ለዘላለም ይኖራል ከኢሳ11፥4-5፤45፥8፤ዳን9፥24 ጋር ያነጻጽሩ። *በተስፋ ቃሉ፤* በኢሳ 65፥17፤66፥22 አዲስ ሰማይና አዲስ ምድር እንደሚሰጡ ተስፋ ተሰጥቶአል። ይኸው ተስፋ በራእ21፥1 ላይ ዳግም ተሰጥቶ እናገኘዋለን።

3፥14 *ያለ ነውርና ያለ ነቀፋ፤* እነዚህ ሁለት ቃላት ክርስቶስን አስመልክተው ጥቅም ላይ ከዋሉበት ከ1ጴጥ 1፥19 ጋር ያነጻጽሩ። *ከእርሱ ጋር በሰላም እንድትገኙ፤* አማኞች በእምነት ስለ ጸደቁ ከእግዚአብሔር ጋር ሰላም አላቸው (ሮሜ5፥1)፤ ነገር ግን እግዚአብሔርን ደስ በማያሰኝ ሕይወት ቢኖሩ፣ እርሱን ሲያሳዝኑና ጌታ በሚመለሰበትም ቀን ምስጋናንና ወሮታን ላያገኙ ይችላሉ (ከ1ቆሮ3፥10-15፤2ቆሮ5፥10 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥15 *የጌታችን ትዕግሥት..... እንድትድኑ፤* ቍ9 ይመ። *ወንድማችን ጳውሎስ፤* ጴጥሮስ ስለ ጳውሎስ የተናገረው በጋለ ስሜት ነው፤ በዐላማቸውና በትምህርታቸው አንድነት እንዳላቸው በጳውሎስ መልእክቶችና በሐዋርያት ሥራ ውስጥ ጎልቶ ይታያል፤ እዚህም ላይ ጴጥሮስ ይህንኑ ያረጋግጣል። ጳውሎስ ለሁለተኛው ጴጥሮስ ተደራሲያን የጻፈላቸው መልእክት ለየስፍራው ባሉ አብያተ ክርስቲያናት እንዲነበብ የተላከውን የሮሜን መልእክት እንደ ሆነ ይታመናል (ከሮሜ16፥4 ጋር ያነጻጽሩ፤ ለሮሜ መልእክት መግቢያ ላይ፣ "ተደራሲያን" የሚለውን ርእስ ይመ፤ እንዲሁም፡ የ1ጴጥ 1፥1 ማብ ይመ ።

3፥16 *በመልእክቶቹ ሁሉ ጽፎአል፤* ምናልባት ጴጥሮስ ይህን ሲል የቅድስናን ሕይወት ለሚመለከት በቍ 11-14 ላይ የሰጣቸውን ትምህርቶች የሚያመለክት ሊሆን ይችላል፤ እነዚህ ምስክሮች ለብዙ መንገድ ከጳውሎስ መልእክቶች ጋር ይመሳሰላሉ። *ዕውቀት የጐደላቸውና ጽናት የሌላቸው ሰዎች፤* ዕውቀት የጐደላቸው የተባሉት፣ ያልተማሩና የሐዋርያትን መሠረታዊ ትምህርት ያልተረዱ፣ በቀላሉም ወደ ስሕተት ትምህርት የሚሄዱትን ሰዎች የሚያመለክት ነው (ከ2፥14 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሌሎችን ቅዱሳት መጻሕፍት፤* ጴጥሮስ የሐዋርያው ጳውሎስን ጽሑፎች የእግዚአብሔር እስትንፋስ ከሆኑት ከብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ጋር እኩል ሥልጣን እንዳላቸው አረጋግጦአል (1፥21፤ 2ጢሞ 3፥16 ይመ)።

3፥17 *ይህን አስቀድማችሁ ስላወቃችሁ፤* ሐሰተኛ መምህ

[18]ነገር ግን በጌታችንና በአዳኛችን በኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋና ዕውቀት እደጉ፤ ለእርሱ አሁንም፣ ለዘላለምም ክብር ይሁን፤ አሜን።

3፥18 ሮሜ3፥24፤ 11፥36፤2ጴጥ1፥2፡11 ፤2፥20

ራን እንደሚመጡ ማለት ነው (ከም 2 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥18 *በ...ዕውቀት እደጉ፤* ጴጥሮስ መልእክቱን የሚደመድመው የዕውቀት አስፈላጊነትን ዳግም አበክሮ በመግለጽ ነው (1፥2-3 እና ማብ ይመ ፤ እንዲሁም 1፥5 ይመ)፤ ይህም ልዩ ዕውቀት አለን ብለው የሚታበዩትን የሐሰተኛ መምህራን ትምህርት ከንቱ ለማድረግ ክርስቲያኖች ኢየሱስን በማወቅ እንዲጐለብቱ ለማበረታታት ነው።

# የሐዋርያው ዮሐንስ መልእክት – አንደኛ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

የመልእክቱ ጸሐፊ፣ የዮሐንስን ወንጌል እንዲሁም አቡቀለምሲስ የተባለውን የራእይ መጽሐፍ የጻፈው የዘብዴዎስ ልጅ ሐዋርያው ዮሐንስ ነው (ማር1፥19-20፤ ከሁለቱም መጻሕፍት መግቢያዎች ላይ "ጸሐፊው" የሚለውን ይመ)። ዮሐንስ ዓሣ አጥማጅ ነበር፤ እርሱ ያዕቆብና ጴጥሮስ ከሌሎቹ ሐዋ ርያት ይበልጥ ለጌታ ቅርቦቹ ነበሩ፤ "ኢየሱስ የሚወደው ደቀመዝሙር" የተባለውም (ዮሐ13፥23) ይህ ሐዋርያ ነው።

የዮሐንስ መልእክት አንደኛን ማን እንደ ጻፈው ራሱ ባለመናገሩ፣ ከቀሩት የአዲስ ኪዳን መልእክቶች ይለያል፤ ስለ ዮሐንስ የተሰጠው የመጀመሪያው ምስክርነት የተገኘው ከቤተ ክርስቲያን አባቶች ነው። ሔሬኔዎስ (140-203 ዓ.ም)፣ የእስክንድርያው ቀለሚንጦስ (155-215 ዓ.ም)፣ ጠርጡ ልያን (150-222 ዓ.ም) እና እርጌንስ (185-253 ዓ.ም) የመጽሐፉ ጸሐፊ ሐዋርያው ዮሐንስ እንደ ሆነ መስክረዋል፤ በጥንታዊት ቤተ ክርስቲያን ከእርሱ በቀር የዚህ መጽሐፍ ጸሐፊ እከሌ ነው ተብሎ ስሙ የተወሣ ሌላ ሰው የለም።

ከላይ የተሰጠው ትውፊታዊ መረጃ በራሱ በመልእክቱም የተደገፈ ነው። ለምሳሌ:-

1 የዮሐንስ ወንጌል የአጻጻፍ ስልት ከዚህ መልእክት ጋር በእጅጉ ይመሳሰላል። ሁለቱም ቀላል በሆነ የግሪክ ቋንቋ የተጻፉ ሲሆን፣ እንደ ብርሃንና ጨለማ፣ ሕይወትና ሞት፣ እውነትና ውሸት፣ ፍቅርና ጥላቻ ያሉትን ተነጻጻሪ ቃላት ይዘው ይገኛሉ።

2 ከዚህ በታች በተጠቀሱት ምንባቦች ውስጥ የሚገኙት ተመሳሳይ ሐረጎችና አገላለጾች የጽሑፎቹን ተመሳሳይነት በጕልሕ ያሳያሉ።

| 1ኛ ዮሐንስ | የዮሐንስ ወንጌል |
|---|---|
| 1፥1 | 1፥1:14 |
| 1፥4 | 16፥24 |
| 1፥6-7 | 3፥19-21 |
| 2፥7 | 13፥34-35 |
| 3፥8 | 8፥44 |
| 3፥14 | 5፥24 |
| 4፥6 | 8፥47 |
| 4፥9 | 1፥14:18፤3፥16 |
| 5፥9 | 5፥32:37 |
| 5፥12 | 3፥36 |

3 ዮሐንስ የክርስቶስ የዐይን ምስክር እንደነበረ መገለጹ (1፥1-4)፣ ክርስቶስ ገና አገልግሎቱን ከመጀመሩ አንሥቶ ተከታዩ መሆኑን ከሚያውሣው ክፍል ጋር አብሮ የሚሄድ ነው።

4 መልእክቱ ከመጀመሪያ አንሥቶ እያንዳንዱ ክፍል በሥልጣን ጀምሮ (በማዘዝ 2፥15:24:28፤ 4፥1፤5፥21፤ በማመልከት 2፥6፤3፥14፤4፥12፤ስሕተትን በመጠቈም 1፥6:8፤2፥4:22) በሥልጣን የመጨረሱ ሁኔታ፣ ከአንድ ሐዋርያ የሚጠበቅ ነገር ነው።

5 ተደራሲያኑን "ልጆቼ ሆይ" ማለቱ (2፥1:28፤3፥7)፣ ዮሐንስ መጻሕፍቱን በጻፈ ጊዜ በዕድሜ የገፋ አረጋዊ መሆኑን ያመለክታል። ይህም፣ የጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ስለ ዕድሜው በትውፊት ካስተላለ ፈችልን ጋር የሚመሳሰል ነው።

6 መናፍቃን የክርስቶስ ተቃዋሚዎች (2፥18)፣ ሐሰተኞች (2፥22) እና የዲያብሎስ ልጆች (3፥10) ተብለው መቅረባቸው፣ ኢየሱስ ዮሐንስን "የነጐድጓድ ልጅ" (ማር3፥17) ማለቱ በትክክል መሆኑን ያረጋግጣል።

7 ዮሐንስ ለጌታ ቅርብ መሆኑን የሚያመለክቱት ክፍሎች (1፥1፤2፥5-6:24:27-28)፤ "ኢየሱስ ይወደው የነበረ ደቀ መዝሙር" እና "ወደ ኢየሱስ ደረት ተጠግቶ ተቀምጦ ነበር"፣ (ዮሐ13፥23)፣ የሚሉት ሐረጎች ትክክል መሆናቸውን ይገልጻሉ።

### መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ

መልእክቱ የተጻፈበትን ጊዜ በትክክል ማስቀመጥ አስቸጋሪ ነው፤ ነገር ግን (1) የቀደምት ክርስ ቲያን ጸሐፊዎች (በተለይም ሔሬኔዎስና የእስክንድርያው ቀለሚንጦስ) ምስክርነት (2) የኖስቲኦች ትምህ ርት ቀደምት ቅርጹ በመልእክቱ መወገዙና መንጸባረቁ ነው፤ (3) ዮሐንስ በዕድሜ የገፋ አረጋዊ መሆኑን የሚያመለክቱት ቃላት፣ ጊዜው የመጀመሪያው ምእተ ዓመት መጨረሻ አካባቢ እንደሆነ ይጠቁማሉ። የ1ኛ ዮሐንስ ጸሐፊ መልእክቱን በአራተኛው ወንጌል መሪ ሐሳብና ዐቢይ ዐላማ ላይ ገንብቶ ያንኑ የሚያዳብር ስለሚመስል (1ዮሐ2፥7-11 ይመ)፣ መልእክቱ የተጻፈው ከ85-95 ዓ.ም ባለው ጊዜ ውስጥ

(በ85 ዓ.ም ሳይጻፍ እንዳልቀረ የሚታመነው የዮሐንስ ወንጌል ከተጻፈ በኋላ) ሳይሆን እን ዳልቀረ ይገመታል።

## የመልእክቱ ተደራሲያን

ይህ መልእክት ቀደም ብለው ላመኑ ክርስቲያኖች እንደ ተጻፈ በ1ዮሐ2፥12-14:19፤3፥1፤5፥13 ተገልጸአል። ነገር ግን ሰዎቹ አነማን እንደሆኑና የት እንደ ነበሩ ፍንጭ አይሰጥም። የማንንም ሰም አለመጥቀሱ በተለያየ ሰፍራ ይኖሩ ለነበሩ ክርስቲያኖች የተጻፈ ዘዋሪ ደብዳቤ። መሆኑን ይጠቁ ማል። ሐዋርያው ዮሐንስ አብዛኛውን የመጨረሻ ሕይወት ዘመኑን (70-100 ዓ.ም) ያሳለፈው፣ በኤፌሶን መሆኑን የጥንት ክርስቲያኖች ጽሑፍ ያሰረጻል። 1ኛ ዮሐንስ ለመጀመሪያ ጊዜ አገልግሎት ላይ የዋለው በእስያ (የዛሬዋ ቱርክ) አውራጃ በኤፌሶን ከተማ ነበር። ዮሐንስ በእስያ አውራጃ በሚገኙ አብያተ ክርሰቲያናት እየተዘዋወረ ያሰተምር እንደ ነበረ የአሰክንድርያው ቀለሚንጦስ ጽፎአል፤ ሰለዚህ መልእክቱ በእስያ ወዳሉት አቢያተ ክርሰቲያናት የተላከ መሆኑን መገመት ይቻላል።

## የኖስቲሳውያን ትምህርት

ቤተ ክርስቲያን ባሳለፈችው ሁለት ምእተ ዓመት ውሰጥ እጅግ አደገኛ ከሆኑት የኑፋቄ ትምህ ርቶች አንዱ ኖስቲሲዝም የሚባለው ነው። የኖስቲሳውያንም ዋና ትምህርት፣ ረቂቅ የሆነው መንፈስ ሁሉ ቅዱስ ነው፤ ሥጋ ሁሉ ደግሞ ርኵሰ ነው የሚል ነው። ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ከሆነ ከዚህ ሁለትዮሽ አሰተሳሰብ አምስት ዋና ዋና ሰሕተቶች ወጥተዋል።

1)ሥጋ የሆነው የሰው አካል የሚዳሰስ፣ የሚጨበጥ በመሆኑ ርኵሰ ነው። ስለዚህ ሙሉ በሙሉ መንፈሰ ከሆነው ከእግዚአብሔር ጋር የሚጻረር ነው። መንፈስ በመሆኑም እግዚአብሔር መልካም ነው።

2) መዳን ከሥጋዊ አካል ማምለጥ ነው፤ ይህም ክርስቶስን በማመን የሚገኝ ሳይሆን ልዩ በሆነ ዕውቀት የሚገኝ ነው ("ዕውቀት" በግሪኩ "ኖሲሰ" ማለት ሲሆን ኖስቲሲዝም የሚለውም ቃል ከዚሁ ይወጣል)።

3) የክርሰቶሰ በእውነት ሥጋ መልበሰ በሁለት መልክ ተክዶአል፤ ሀ) ዶሴቲዝም የሚለውን አመለ ካከት የሚከተሉ ወገኖች፣ ክርሰቶሰ ሥጋ የመሰለ አካል ቢለብስ፣ (ለበስ)እንጂ እውነተኛ ሥጋን አለበሰም ይላሉ። ይህም "ዶኬኦ" (መምሰል) ከሚለው የግሪክ ቃል የመጣ ነው። ለ) ሴሬንቲያኒዝም የሚለውን አመለካከት የሚከተሉ ደግሞ በመለኮታዊ ባሕርይው አምላክ የሆነው ክርስቶስ በጥምቀት ጊዜ ኢየሱስ ከተባለው ሰው ጋር ተጻበለ፤ ኢየሱስ ከመሞቱ በፊት ግን ትቶት ሄደ ይላሉ። ይህም አሰተምህሮ የትምህርቱ ቀንደኛ አፈ ቀላጤ በሆነው በሴሬንቲዩ ሰም የተሰየመ ነው። እንግዲህ 1ኛ ዮሐንስ እንዲጻፍ ምክንያት ለሆኑት ለአብዛኞቹ ነገሮች መሠረቱ ይህ አመለካከት ነው (1፥1፤ 2፥22፤ 4፥2-3 ይመ)።

4) ሥጋ ክፉ ነገር ነው ተብሎ ሰለሚታሰብ መነሳቀል አለበት። ይህ የገዳማዊ ኑሮ መልክ ያለው የኖስቲሳውያን ትምህርት ለቈላሰይሰ መልእክት መጻፍ አንዱ ምክንያት (ቈላ2፥21-23) ነው።

5) ይህ የሁለትዮሽ አመለካከት በሌላም በኩል የሥነ ምግባር ብልሽት አሰከትሎአል። ክፉ ነገር የእግዚአብሔርን ሕግ መጣሰ (1ዮሐ3፥4) ሳይሆን፣ ክፉ ነገር ማለት ራሱ ሥጋ ነው፤ ሰለዚህ የእግዚአብሔርን ሕግ መጣስ በሞራል ረገድ አንዳች መዘዝ አያስከትልም የሚል እምነት አላቸው።

እንደ እውነቱ ከሆነ በአዲሰ ኪዳን የተጠቀሰው ኖሰቲሲዝም ገና እንጭጭ ኑፋቄ ነበር፤ ወደ ውሰብሰብነት ደረጃ የደረሰው በሁለተኛውና በሦስተኛው ምእተ ዓመት ላይ ነው። ይህ የመጀመሪያው የኖስቲሳውያን ኑፋቄ፣ በቈላሰይስና በዮሐንስ መልእክቶች የተወሣ ብቻ ሳይሆን በዚያን ጊዜ መኖሩ፣ በ1ኛና በ2ኛ ጢሞቴዎስ፣ በቲቶና በ2ኛ ጴጥሮስ፣ ምናልባትም በ1ኛቆሮንቶሰ መልእክት ውሰጥ ሳይን ጸባረቅ አልቀረም።

## የተጻፈበት ወቅትና ዐላማ

የዮሐንሰ አንባቢዎች በወቅቱ ከነበረው የሴሬንትያን ኖሰቲሳውያን (የኖሰቲሳውያን ትምህርት ይመ) ጋር ግንባር ለግንባር ተጋፍጠዋል። ይህ የሰሕተት ትምህርት ከልክ ያለፈ ልቅ ነጻነትን ከማወጁ የተነሣ የሥነ ምግባር ሕጎችን አሽቀንጥሮ የጣለ ነበር። ሰለዚህ ዮሐንሰ ይህን መልእክት ሲጽፍ በሁለት መሠረ ታዊ ነገሮች ላይ አነጣጥሮአል፤

1) ሐሰተኞቹን መምህራን ማጋለጥ (2፥26)
2) አማኞች ደግሞ የድነትን ማረጋገጫ እንዲያውቁ ማድረግ (5፥13)።

ዮሐንስ ከኖሰቲሶች ጋር ኀይለኛ ግብ ግብ በመግጠም በተለይ የሥነ ምግባር ጒድለታቸውን መኻል አናቱን መትቶ ጥሎታል (3፥8-10)። ክርስቶስ በዚች ምድር ላይ በሥጋ ስመገለጡ እርሱ ራሱ የዐይን ምሰክር መሆኑን በመግለጥ አንባቢዎቹ ሥጋ ለብሶ በእውነት ሰው የሆነውን ክርስቶስን በማመን እንዲድኑ ያለውን ፍላጎት ይገልጻል (1፥3)፤ ይህ ከተሳካለት፣ ለጸሐፊው ታላቅ ደሰታ ነው (1፥4)።

## አስተዋፅኦ

1. መግቢያ፤ የክርሰቶሰ ሥጋ መልበሰ እርግጠኝነት (1፥1-4)

2. የክርስትና ሕይወት ከአብና ከወልድ ጋር የሚደረግ ኅብረት ነው (1፥5-2፥28)
   ሀ) በኅብረቱ ላይ የሚደርስ የግብረ ገብነት ፈተና (1፥5-2፥11)
      1) የሥነ ምግባር መመሳሰል (1፥5-7)
      2) ኃጢአትን መናዘዝ (1፥8-2፥2)
      3) መታዘዝ (2፥3-6)
      4) በምእመናን መካከል መኖር የሚገባው ፍቅር (2፥7-11)
   ለ) ሁለት ዐይነት ማፈግፈግ ወይም ወደኋላ መመለስ (2፥12-17)
   ሐ) ኅብረትን ከክርስቶስ አኳያ መፈተን (2፥18-28)
      1) ከሐዲዎችን ከአማኞች ጋር ማነጻጸር (2፥18-21)
      2) የክርስቶስ ማንነት፤ ዋናው ጥያቄ ይህ ነው (2፥22-23)
      3) ከክርስቶስ ጋር ያለው ኅብረት እስከመጨረሻው እንዲዘልቅ ጽኑ እምነት ማስፈለጉ (2፥24-28)
3. ክርስቲያንነት የእግዚአብሔር ልጅ መሆን ነው (2፥29-4፥6)
   ሀ) የእግዚአብሔር ልጆች መሆናችን የሚለካው በግብረ ገብነታችን ነው (2፥29-3፥24)
      1) ጽድቅ (2፥29-3፥10ሀ)
      2) ፍቅር (3፥10ለ -24)
   ለ) ተቃዋሚዎችን በክርስቶስ ልጅነት ጉዳይ መፈተን (4፥1-6)
4. ክርስትና የሥነ ምግባርና የክርስቶስን ማንነት የመረዳት ውሕደት መሆኑ (4፥7-5፥12)
   ሀ) የሥነ ምግባር ፈተና፤ ፍቅር (4፥7-5፥12)
      1) የፍቅር ምንጩ (4፥7-16)
      2) የፍቅር ፍሬው (4፥17-19)
      3) አንድ አማኝ ከእግዚአብሔርና ከሌላው አማኝ ጋር ያለው ግኑኝነት (4፥20-5፥1
      4) መታዘዝ:- የእግዚአብሔር ልጆች መታወቂያ ምልክታቸው ፍቅር ነው (5፥2-5)
   ለ) ስለ ክርስቶስ ማንነት የሚቀርብ ፈተና (5፥6-12)
5. መደምደሚያ ታላላቅ የክርስቲያን እርግጦች (5፥13-21)

## የሕይወት ቃል

**1** ስለ ሕይወት ቃል ከመጀመሪያው የነበረውን፣ የሰማነውን፣ በዐይኖቻችን ያየነውን፣ የተመለከትነውንና እጆቻችን የዳሰሱትን እንናገራለን። [2]ሕይወት ተገለጠ፤ እኛም አይተነዋል፤ እንመሰክርለታለንም። በአብ ዘንድ የነበረውን፣ ለእኛም የተገለጠልንን የዘላለም ሕይወት እንነግራችኋለን፤ [3]እናንተም ከእኛ ጋር ኅብረት እንዲኖራችሁ፣ ያየነውንና የሰማነውን እንነግራችኋለን፤ ኅብረታችንም ከአብ፣ ከልጁም ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋር ነው። [4]ደስታችንም[ሀ] ፍጹም ይሆን ዘንድ ይህን እንጽፍላችኋለን።

## በብርሃን መመላለስ

[5] ከእርሱ የሰማነው ለእናንተም የምንነግራችሁ መልእክት፣ እግዚአብሔር ብርሃን ነው፤ ጨለማም በእርሱ ዘንድ ከቶ የለም የሚል ነው። [6]በጨለማ እየተመላለስን ከእርሱ ጋር ኅብረት አለን ብንል እንዋሻለን፤ እውነትንም አንኖረውም። [7]ነገር ግን እርሱ በብርሃን እንዳለ፣ እኛም በብርሃን ብንመላለስ እርስ በእርሳችን ኅብረት አለን፤ የልጁም የኢየሱስ ክርስቶስ ደም ከኃጢአት ሁሉ[ለ] ያነጻናል።

[8]ኃጢአት የለብንም ብንል፣ ራሳችንን እናስታለን፤ እውነትም በእኛ ውስጥ የለም። [9]ኃጢአታችንን ብንናዘዝ ኃጢአታችንን ይቅር ሊለን፣ ከዐመፃ ሁሉ ሊያነጻን እርሱ ታማኝና ጻድቅ ነው። [10]ኃጢአት አልሠራንም ብንል፣ እርሱን ሐሰተኛ እናደርገዋለን፤ ቃሉም በእኛ ውስጥ የለም።

**2** ልጆቼ ሆይ፤ ይህን የምጽፍላችሁ ኃጢአት እንዳትሠሩ ነው፤ ነገር ግን ማንም ኃጢአት ቢሠራ፣ በአብ ዘንድ ጠበቃ አለን፤ እርሱም ጻድቁ ኢየሱስ ክርስቶስ ነው። [2]እርሱም የኃጢአታችን ማስተስረያ ነው፤ ይኸውም[ሐ] ለዓለም ሁሉ ኃጢአት እንጂ ለእኛ ብቻ አይደለም።

1፥1 ሉቃ24፥48፤ ዮሐ1፥2፡14፡19፥35፤20፥27፤ሐሥ4፥20፡ 2ጴጥ1፥16፤ 1ዮሐ4፥14
1፥2 ማቴ25፥46፤ ዮሐ1፥1-4፡11፥25፤ 14፥6፤15፥27፤ቲቶ 3፥16፡1ጴጥ1፥20፡ 1ዮሐ3፥5፡8፤4፤11፥25 ፡14፥6፡15፥27፤ቲቶ 3፥16፡1ጴጥ1፥1፥20፡ 1ዮሐ3፥5፡8
1፥3 ቍ1፤1ቆሮ1፥9
1፥4 ዮሐ3፥29፡ 1ዮሐ2፥11
1፥5 1ጢሞ6፥16፤ 1ዮሐ3፥11
1፥6 ዮሐ3፥19-21፤ 8፥12፤2ቆሮ6፥14፤ ኤፌ5፥8፡1ዮሐ2፥4፡ 11፤4፥20
1፥7 ኢሳ2፥5፡ዕብ9፥14 ፤ራእ1፥5፤7፥14
1፥8 ምሳ20፥9፤ ኤር2፥35፤ዮሐ8፥44፤ ሮሜ3፥9-19፤ያዕ3፥2 ፡1ዮሐ2፥4
1፥9 ቍ7፡መዝ 32፥5፤51፥2፡ምሳ 28፥13፤ሚክ7፥18-20 ፤ዕብ10፥22

1፥10 ቍ8፤ዮሐ5፥38ዮሐ5፥38፤1ዮሐ2፥14፤5፥10 2፥1 ቍ12፡13፡ 28፤ሮሜ8፥34፡1ተሰ2፥11፡1ጢሞ2፥5፡1ዮሐ3፥7፡18 ፡4፥4፡5፥21
2፥2 ማቴ1፥21፡ ዮሐ3፥17፤ሮሜ 3፥25፤1ዮሐ4፥10፤ሚኪ7፥18-20

[ሀ]4 አንዳንድ ቅጆች *የእናንተ* ይላል
[ለ]7 ወይም *ከማንኛውም*
[ሐ]2 *ኃጢአታችንን አስወግዶ የእግዚአብሔርን ቍጣ ከእኛ የሚያርቅ እርሱ ነው፤ ይኸውም የእኛን ኃጢአት ብቻ ሳይሆን ማለትም ነው።*

*1፥1-4፤* የዚህ መልእክት መግቢያ እንደ ዮሐንስ ወንጌል መግቢያ ተመሳሳይ ርእሶችንና ቃላትን ይጠቀማል (1፥1-4)፤ እነርሱም፣ "*መጀመሪያ*"፣ "*ቃል*"፣ "*ሕይወት*" እና "*ጋር*" የሚሉት ናቸው።

1፥1 *ስለ ሕይወት ቃል፤* ሕይወት የሆነውንና ሕይወትን የገለጠውን ያሳያል (ቍ 2 እና ማብ ይመ)። *ቃል፤* እዚህ ቦታ ላይ "ቃል" መገለጥን ያመለክታል (ዮሐ 1፥1 ማብ ይመ)። *ከመጀመሪያው የነበረውን፤* ከጥንት ጀምሮ ነበር። *የሰማነውን ... ያየነውን፣ የተመለከትነውንና ... የዳሰሱትን፤* ሐዋርያው ስለ ሕይወት ቃል ጥንቃቄ የተሞላበት፣ ተገቢ የሆነ ግንዛቤን ወስዷል። ዘላለማዊ የነበረው፣ "ሥጋ ሆነ" ሲል መስክሯል (ዮሐ 1፥14)፤ ይህም ሥጋና ደም የሆነ ሰው ሆነ ማለት ነው። እርሱ እውነተኛ አምላክና እውነተኛ ሰው ነው። ዮሐንስ ከመጀመሪያው እንሥቶ ኖስትስ የሚባለውን የሐሰት ትምህርት ይቃወማል። በመግቢያው ሥር፣ "የኖስትሳውያን ትምህርት" የሚለውን ይመ። *እንናገራለን፤* ዮሐንስንና ሌሎች ሐዋርያትን ያመለክታል።

1፥2 *ሕይወት ... የዘላለም ሕይወት፤* ክርስቶስን ማለት ነው። በራሱ ሕይወት ያለውና ሕያው ስለ ሆነ፣ "ሕይወት" ተብሎ ተጠራ (ዮሐ11፥25፤ 14፥6)። እርሱ የሕይወት ምንጭና በሕይወት ላይ ሥልጣን ያለው ነው (5፥11)። መልእክቱ ዘላለማዊ ሕይወትን መሪ ሐሳብ አድርጎ ያቀርባል (5፥20)። *የዘላለም ሕይወት፤* ዮሐንስ የዘላለም ሕይወትን ከክርስቶስ እንጻር ይፈታዋል፤ ይህም በክርስቶስ ላይ ባለ እምነትና ከእርሱም ጋር በሚኖረው ኅብረት ብቻ የሚገኝ ነው (ቍ 2፡6-7፤ 2፥22-25፤ 5፥20)።

1፥3 *ከእኛ ጋር ኅብረት እንዲኖራችሁ፤* ሥጋ የሆነውን ክርስቶስ በመስማታቸው፣ በማየታቸውና በመዳሰሳቸው የተገኘውን ልምድ መካፈልን ያሳያል (ቍ1)። "ኅብረት" የሚለው ቃል በግሪኩ፣ "ኮይኖኒያ" ማለት ሲሆን፣ ትርጕሙም አማኞች ከክርስቶስ ጋር ያላቸውን መንፈሳዊ ኅብረት የሚያመለክት ነው፤ ይኸውም የወይን ግንድ ከቅርንጫፉ ጋር እንዲሁም በራስና በተቀረው አካል መካከል (1ቆሮ 12፥12፣ ቈላ1፥18፤ ዮሐ15፥1-5) ባለው ግኑኝነት ተመስሎአል፤ እንዲሁም አማኞች ከእግዚአብሔር ጋር እና እርስ በርስ ያላቸውን ግኑኝነት ያመለክታል።

1፥4 *ደስታችንም ፍጹም ይሆን ዘንድ፤* የዮሐንስ ደስታ ሙሉ የሚሆነው፣ ተደራሲያኑ እንደ እርሱ እውነተኛውን የክርስቶስ ዕውቀት ሲያገኙ ብቻ ነው (2ዮሐ12 ይመ)።

1፥5 *ከእርሱ፤* ከክርስቶስ ማለት ነው። *ብርሃን ... ጨለማ፤* "ብርሃን" የሚለው ቃል መልካም፣ እውነትና ቅዱስ የሚለውን ሲወክል፣ "ጨለማ" የሚለው ቃል ደግሞ ክፉና ሐሰት የሆነውን ይወክላል (ዮሐ3፥9-21)።

1፥6-7 *በጨለማ እየተመላለስን ... በብርሃን ብንመላለስ፤* ለየቅል የሆኑ ሁለት የኑሮ ዘይቤዎችን ይገልጻል፤ አንደኛው የኃጢአትና የስሕተት ኑሮ ሲሆን፣ ሌላኛው ደግሞ የእውነትና የቅድስና ኑሮ ነው።

1፥6 *እየተመላለስን፤* ኑሮን የሚያመለክት ተለዋጭ ዘይቤ ነው። *ከእርሱ ጋር ኅብረት፤* ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት እያደረጉ መኖርን የሚያመለክት ነው። *አለን፤* ዮሐንስንና ተደራሲያኑን የሚያመለክት ነው። *እውነትንም፤* ዮሐ1፥14 ማብ ይመ።

1፥7 *የኢየሱስ ክርስቶስ ደም ከኃጢአት ሁሉ ያነጻል፡* የኢየሱስ ደም በአማኝ ሕይወት ውስጥ ባለማቋረጥ የሚያከናውነውን ከኃጢአት የማንጻት ሥራ ያሳያል። *ከኃጢአት፤* በ1ዮሐንስ ውስጥ የሚገኝ ዐቢይ ቃል ነው፤ በግሪኩ ቃሉ 27 ጊዜ ተጠቅሶአል።

1፥9 *ይቅር ሊለን፤* ሰው ከእግዚአብሔር ጋር የነበረውንና በኃጢአት ምክንያት ያጣውን ኅብረት እግዚአብሔር እንደሚያድስ የሚያመለክት ነው (ማቴ 6፥12)። *ታማኝና ጻድቅ፤* ይህ ሐረግ፣ እግዚአብሔር ኃጢአታ ቸውን ለሚናዘዙ ሁሉ እንደ ባሕርዩና እንደ ጸጋው መጠን ለሕዝቡ የሚያደርገውን ርኅራኄ ያሳያል (መዝ 143፥1፤ ዘካ 8፥8)። *ታማኝና፤* ይቅርታ ለማድረግ ለሰጠው ተስፋ ማስት ነው (ኤር 31፥34፤ ሚክ 7፥18-20፤ ዕብ 10፥22-23)።

1፥10 *ኃጢአት አልሠራንም ብንል፡* ኖስቲሶች እኩይ ምግባራቸው ኃጢአት እንደ ሆነ አያምኑም።

2፥1 *ልጆቼ ሆይ፤* በእድሜ ባለጸጋ የሆነው ዮሐንስ፣ ይህን የመሰለ የፍቅር ገለጻ ብዙ ጊዜ ይጠቀማል (ቍ 12-13፡28፤ 3፥7፤ 18፤ 4፥4፤ 5፡21)። *ኃጢአት እንዳትሠሩ፤* ዳግመኛ የተወለዱ አማኞች ኃጢአት ሊሠሩ እንደሚችሉ ዮሐንስ ያምናል፤ ነገር ግን ክርስቲያን ኃጢአት መሥራት አለበት ብሎ አያስተምርም፤ ይልቁንም ተደራሲያኑ ከኃጢአት ተለይተው እንዲኖሩ ይመክራል። *ጠበቃ አለን፤* በችሎት ፊት እኛን ወክሎ የሚቆም ማለት ነው (የዮሐ 14፥16 ማብ ይመ)። *ጻድቁ፤* በእግዚአብሔር ችሎት ፊት ጠበቃው ኃጢአት የሌለበት ሲሆን ይገባዋል፤ እርሱም እንደዚያው ነው።

2፥2 *የኃጢአታችን ማስተስረያ፤* አማራጭ ትርጕሙ ከግሪኩ በቀጥታ የተወሰደ ነው (4፥10 ይመ)፤ የእግዚአብሔር ቅድስና፣ ሰው በሠራው ኃጢአት እንዲቀጣ ይጠይቃል። ስለዚህ እግዚአብሔር ከፍቅሩ የተነሣ (4፥10፤ ዮሐ 3፥16) ልጁ ኢየሱስ የአማኞችን ኃጢአት ያስተሰርይ ዘንድ ላከው። በክርስቲያኖች ኃጢአት ላይ እግዚአብሔር የነበረው ቍጣ ተወግዶ ስክርስቶስ ላይ ስላረፈ፣ የእግዚአብሔር ቍጣ በርዶአል ማስት ነው። በዚህ መንገድ የእግዚአብሔር ቍጣ በርዶአል (ሮሜ 3፥25 ማብ ይመ)። *ለዓለም ሁሉ ኃጢአት፤* በክርስቶስ መሥዋዕትነት የሚገኘው የኃጢአት ይቅርታ፣ ለአንድ ወገን ብቻ የተወሰነ ሳይሆን ዓለም ዐቀፍ እድማስ አለው (ዮሐ 1፥29)። ሆኖም ግን የዚህ ድነት ተጠቃሚ መሆን የሚቻለው በእምነት ሲቀበሉት ብቻ ነው (ዮሐ 3፥16)፤ ይህ ክፍል በመጨረሻው ቀን ሰው ሁሉ ይድናል የሚለውን ትምህርት የሚደግፍ

[3]ትእዛዛቱን ብንፈጽም እርሱን ማወቃችንን በዚህ እርግጠኞች እንሆናለን:: [4]"እርሱን ዐውቃለሁ" እያለ ትእዛዙን የማይፈጽም ግን ሐሰተኛ ነው፤ እውነትም በእርሱ ውስጥ የለም:: [5]ነገር ግን ማንም ቃሉን ቢጠብቅ፣ በእውነት የእግዚአብሔር ፍቅር[m] በእርሱ ፍጹም ሆኖአል:: በእርሱ መሆናችንን የምናውቀው በዚህ ነው፤ [6]ማንም በእርሱ እኖራለሁ የሚል፣ ኢየሱስ እንደ ተመላለሰ ሊመላለስ ይገባዋል::

[7]ወዳጆች ሆይ፤ የምጽፍላችሁ ከመጀመሪያ የነበራችሁን የቈየውን ትእዛዝ እንጂ አዲስ ትእዛዝ አይደለም፤ የቈየው ትእዛዝ የሰማችሁት ቃል ነው:: [8]በሌላ በኩል የምጽፍላችሁ ጨለማው ዕያለፈና እውነተኛው ብርሃን እየበራ ስለ ሆነ፣ በእርሱም፣ በእናንተም ዘንድ እውነት የሆነውን አዲስ ትእዛዝ ነው:: [9]በብርሃን አለሁ የሚል፣ ወንድሙን ግን የሚጠላ እሁንም በጨለማ ውስጥ አለ:: [10]ወንድሙን የሚወድ በብርሃን ይኖራል፤ በእርሱም ዘንድ የመሰናከያ ምክንያት የለውም:: [11]ነገር ግን ወንድሙን የሚጠላ በጨለማ ውስጥ ነው፤ በጨለማ ይመላለሳል፤ ጨለማው ስላሳወረውም የት እንደሚሄድ አያውቅም::

[12]ልጆች ሆይ፤
ኀጢአታችሁ ስለ ስሙ ተሰርዮላችኋልና፣
እጽፍላችኋለሁ::
[13]አባቶች ሆይ፤
ከመጀመሪያ ያለውን እርሱን
ዐውቃችሁታልና፣
እጽፍላችኋለሁ::
ጐበዛዝት ሆይ፤ ክፉውን አሸንፋችኋልና፣
እጽፍላችኋለሁ::
ልጆች ሆይ፤
አብን ዐውቃችሁታልና፣
እጽፍላችኋለሁ::
[14]አባቶች ሆይ፤
ከመጀመሪያ ያለውን እርሱን
ዐውቃችሁታልና፣
እጽፍላችኋለሁ::
ጐበዛዝት ሆይ፤
ብርቱዎች ስለሆናችሁ፣
የእግዚአብሔር ቃል በእናንተ ስለሚኖር፣
ክፉውንም ስላሸነፋችሁ፣
እጽፍላችኋለሁ::

## ዓለምን አትውደዱ

[15]ዓለምን ወይም በዓለም ያለውን ማንኛውንም ነገር አትውደዱ፤ ማንም ዓለምን ቢወድ የአብ ፍቅር በእርሱ ዘንድ የለም፤ [16]ምክንያቱም በዓለም ያለው ሁሉ:- የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮትና የኑሮ ትምክሕት ከዓለም እንጂ ከአብ የሚመጣ አይደለም:: [17]ዓለምና ምኞቱ ያልፋሉ፤ የእግዚአብሔርን ፈቃድ የሚፈጽም ግን ለዘላለም ይኖራል::

## ከክርስቶስ ተቃዋሚዎች መጠንቀቅ

[18]ልጆች ሆይ፤ ይህ የመጨረሻው ሰዓት

[m]5 ወይም ለእግዚአብሔር ያለው ፍቅር ማለት ነው::

2፥3 ቍ4:5፤ዮሐ 14፥15፤1ዮሐ3፥24፤ 4፥13፤5፥2
2፥4 ቍ3፤ቲቶ1፥16 ፤1ዮሐ1፥6:8፤3፥6፤ 4፥7:8
2፥5 ቍ3፤ዮሐ14፥15 ፤1ዮሐ4፥12
2፥6 ማቴ11፥29
2፥7 ቍ24፤1ቆሮ 10፥14፤1ዮሐ3፥11: 23፤4፥21፤2ዮሐ5:6
2፥8 ዮሐ19፤ 13፥34፤ሮሜ13፥12 ፤ኤፌ5፥8፤1ተሰ5፥5፤ ዕብ10፥25
2፥9 ቍ11፤ዘሌ 19፥17፤1ዮሐ1፥5፤ 3፥10:15:16፤4፥20:21
2፥10 ቍ11፤መዝ 119፥165፤1ዮሐ3፥14
2፥11 ቍ9፤ዮሐ 11፥9፤12፥35፤ 1ዮሐ1፥6
2፥12 ቍ1፤1ዮሐ3፥23
2፥13 ቍ1:14፤ማቴ 5፥37፤ዮሐ1፥1፤16፥33
2፥14 ቍ13፤ዮሐ 1፥1፤5፥38፤ኤፌ6፥10 ፤ዕብ4፥12፤1ዮሐ1፥10
2፥15 ሮሜ12፥2፤ ያዕ4፥4
2፥16 ዘፍ3፥6፤ምሳ 27፥20፤ሮሜ13፥14፤ ኤፌ2፥3
2፥17 ማቴ12፥50፤ ዕብ12፥27
2፥18 ቍ22፤ሮሜ 13፥11፤1ዮሐ4፥1:3፤ 2ዮሐ 7

ሳይሆን፣ እግዚአብሔር የማያዳላ አምላክ መሆኑን የሚያሳይ ነው::

2፥3 *ትእዛዛቱን ብንፈጽም፤* ይህ ሐረግ በሕይወታቸው ሁሉ እግዚአብሔርን በመታዘዝ የሚመሩትን የሚያመለክት ነው::

2፥5 *የእግዚአብሔር ፍቅር በእርሱ ፍጹም ሆኖአል፤* ይህ ሐረግ፣ እግዚአብሔር ለእማኝ ያለው ፍቅር እማኙን ወደ መታዘዝ ሲያመጣው ፍጹም እንደሚሆን (4፥12) ወይም ለእግዚአብሔር ያለን ፍቅር (አማራጭ ትርጕሙን ይመ) በመታዘዝ ሲገለጥ ፍጹም እንደሚሆን ሊያሳይ ይችላል (3፥16-18):: *በእርሱ፤* ከእግዚአብሔር ጋር ያለንን መንፈሳዊ ኅብረት ያሳያል (ዮሐ 17፥21 ይመ)::

2፥7-8 *አዲስ ትእዛዝ* ዮሐ 13፥34-35 ይመ:: በመጽሐፍ ቅዱስ ፍቅርን በተመለከተ የተሰጠው ትእዛዝ ነበር ነው (ዘሌ 19፥18፤ ማቴ 22፥39-40 ይመ):: ነገር ግን አዲስ ሆኖ የታየው:- (1) መለኮታዊ ፍቅር በመስቀል ላይ አዲስ ሆኖ በመገለጡ፣ (2) ክርስቶስ የብሉይ ኪዳንን ሕግ (ማቴ 5 ይመ) በዘመኑ ለነበሩ ሰዎች ሲያብራራ አዲስ ይመስል ነበር፣ እንዲሁም (3) አማኞች እርስ በርስ በነበራቸው ፍቅር በየዕለቱ ያድጉ ስለ ነበረ ነው::

2፥7 *ወዳጆች ሆይ፤* "ልጆቼ ሆይ" (ቍ 1) እንደሚለው ሐረግ፣ ይህም ዮሐንስ አዘውትሮ የሚጠቀምበት ሐረግ ነው (በሁሉቱ መልእክቶቹ ውስጥ ይህን ሐረግ ዐሥር ጊዜ ተጠቅሞበታል (ይኸውም እዚህ ላይ እና 3፥2:21፤ 4፥1:7:11፤ 3ዮሐ1-2:5:11) ነው:: *ከመጀመሪያ፤* ወንጌልን ሰምተው የክርስትናን ሕይወት መኖር ከጀመሩበት ጊዜ ጀምሮ ማለት ነው::

2፥8 *እውነተኛው ብርሃን፤* ይህ ሐረግ በአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ በዚህ ቦታና በዮሐንስ 1፥19 ላይ ብቻ ይገኛል:: ይህም የዓለም ብርሃን የሆነውንና በአማኞች ሕይወት ውስጥ የማዳን ሥራ የሚሠራውን የኢየሱስ ክርስቶስን ወንጌል ያመለክታል::

2፥9-10 *የሚጠላ ... የሚወድ፤* በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ጥላቻና ፍቅር እንደ ስሜት የሚታዩ ሳይሆኑ፣ በተግባር የሚገለጡ ግብረ ገባዊ ባሕርያት ናቸው (3፥15-16)::

2፥9 *በብርሃን... በጨለማ፤* የ1፥5 ማብ ይመ:: *ወንድሙን* እንደ እርሱ እማኝ የሆነውን ማለት ነው::

2፥10 *የመሰናከያ ምክንያት፤* በኀጢአት መውደቅን ያሳያል::

2፥12-14 *ስለ ... እጽፍላችኋለሁ፤* ተደራሲያኑ ጠንካራ ፈተና ውስጥ ቢሆኑም እንኳ፣ ዮሐንስ ድነታቸውን አይጠራጠርም:: *ልጆች ሆይ ... አባቶች ... ጐበዛዝት፤* በዚህ መልእክት "ልጆች ሆይ" የሚለው ሐረግ፣ አባቶችንና ጐበዛዝትን ጨምሮ ተደራሲያኑን ሁሉ የሚያመለክት ነው (የቍ 1 ማብ ይመ):: "አባቶች" እና "ጐበዛዝት" የሚሉት ቃላት ግን፣ ሁለት የመንፈሳዊ እድገት ደረጃዎችን ሊያመለክቱ ይችላሉ:: አንዳንዶች ግን፣ "ልጆች" የሚለውን ጨምሮ፣ ሦስት የመንፈሳዊ እድገት ደረጃዎችን ያሳያል ይላሉ::

2፥12 *ስሙ፤* ኢየሱስ የሚለውን ስም ማለት ነው (3፥23፤ 5፥13 እና ሐሥ 4፥12 ማብ ይመ)::

2፥13-14 *ከመጀመሪያ ያለውን እርሱን፤* ክርስቶስን ማለት ነው (የ1፥1 ማብ ይመ)::

2፥15 *ዓለምን፤* የዓለምን ሕዝብ (ዮሐ3፥16)፣ ወይም ግዑዙን ዓለም (ዮሐ17፥24) የሚያመለክት ሳይሆን፣ እግዚአብሔርንና ጽድቅን የሚቃወመውን፣ በሰይጣን ግዛት ሥር ያለውን ኀጢአተኛ ዓለም ነው (ቍ 16፤ ያዕ 4፥4):: *የአብ ፍቅር፤* አማኞች ለአብ ያላቸውን ፍቅር ያመለክታል::

2፥18 *የመጨረሻው ሰዓት፤* ዮሐንስ እንደ ሌሎቹ የአዲስ ኪዳን ጸሐፍያን፣ ከክርስቶስ የመጀመሪያ መምጣት ጀምሮ ያለውን ጊዜ እንደ መጨረሻዎቹ ቀናት ይመለከተዋል (ሐሥ2፥17፤ 2ጢሞ 3፥1፤ ዕብ1፥2፤ 1ጴጥ1፥20 ይመ):: እነዚህ የአዲስ ኪዳን ጸሓፍያን፣ ይህን ዘመን የቀናቶቹ "መጨረሻ" ነው ያሉበት ምክንያት፣ የድነትን ታሪክ በተመለከተ የቀድሞዎቹ ትንቢቶችም ሆኑ አዲሶቹ መገለጦች ከክርስቶስ ዳግም ምጽአት በፊት ምንም ዐይነት አዲስ ዘመን እንደማይመጣ ስለሚያስገነዝቡ ነው:: የመጨረሻዎቹ "ቀናት"፣ "የመጨረሻዎቹ ዘመናት" እና "የመጨረሻው ሰዓት" በሚሉት ሐረጎች ውስጥ "መጨረሻ" የሚለው ቃል ምጽአቱ በቶሎና በደጅ እንደ ሆነ የሚያመለክት ነው:: ክርስቲያኖች የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ነቅተው መጠበቅ ይኖርባቸዋል (ማቴ25፥1-13):: *የክርስቶስ ተቃዋሚ ... የክርስቶስ ተቃ*

ነው፣ እንደሰማችሁትም የክርስቶስ ተቃዋሚ ይመጣል፤ አሁን እንኳ ብዙ የክርስቶስ ተቃዋሚዎች መጥተዋል፤ የመጨረሻው ሰዓት እንደ ሆነ የምናውቀውም በዚህ ነው።

[19]ከእኛ መካከል ወጡ፤ ይሁን እንጂ ከእኛ ወገን አልነበሩም፤ ከእኛ ወገን ቢሆኑማ ኖሮ ከእኛ ጋር ጸንተው በኖሩ ነበር። ነገር ግን ሁሉም ከእኛ ወገን እንዳልነበሩ ይታወቅ ዘንድ ከእኛ ተለዩ።

[20]እናንተ ግን ከእርሱ ከቅዱሱ፣ ቅባት አላችሁና፤ ሁላችሁም እውነትንᵐ ታውቃላችሁ። [21]እኔ የምጽፍላችሁ እውነትን ስለ ማታውቁ አይደለም፤ ነገር ግን እውነትን ስለምታውቁና ከእውነት ምንም ውሸት ስለ ማይወጣ ነው። [22]ክርስቶስ አይደለም ብሎ ኢየሱስን ከሚክድ በቀር ሐሰተኛ ማነው? ይህ አብንና ወልድን የሚክደው የክርስቶስ ተቃዋሚ ነው። [23]ወልድን የሚክድ ሁሉ አብ የለውም፤ ወልድን የሚያምን ሁሉ አብም አለው።

[24]ከመጀመሪያ የሰማችሁት በእናንተ ውስጥ ይኑር፤ ከመጀመሪያ የሰማችሁት በእናንተ ውስጥ ቢኖር፣ እናንተም በወልድና በአብ ትኖራላችሁ። [25]ይህ እርሱ የሰጠን ተስፋ የዘላለም ሕይወት ነው።

[26]ስለሚያስቷችሁ ሰዎች ይህን ጽፌላችኋለሁ። [27]እናንተ ግን ከእርሱ የተቀበላችሁት ቅባት በውስጣችሁ ይኖራልና ማንም እንዲያስተምራችሁ አያስፈልግም፤ ነገር ግን እውነት እንጂ ሐሰት ያልሆነው የእርሱ ቅባት ስለ ሁሉም ነገር እንደሚያስተምራችሁ፣ ያም እውነት እንጂ ሐሰት እንዳል ሆነ፣ እናንተንም እንዳስተማራችሁ በእርሱ ኑሩ።

## የእግዚአብሔር ልጆች

[28]እንግዲህ ልጆች ሆይ፤ እርሱ ሲገለጥ ድፍረት እንዲኖረን፣ በሚመጣበትም ጊዜ በፊቱ እንዳናፍር በእርሱ ኑሩ።

[29]እርሱ ጻድቅ መሆኑን ካወቃችሁ፣ ጽድቅን የሚያደርግ ሁሉ ከእርሱ እንደ ተወለደ ታውቃላችሁ።

# 3

የእግዚአብሔር ልጆች ተብለን እንድንጠራ አብ እንደምን ያለ ፍቅር ሰጠን! — አብ እትረፍርፎ ያፈሰሰልን ፍቅር ምንኛ ታላቅ ነው! እኛም እንዲሁ ልጆቹ ነን። ዓለም እኛን የማያውቀንም እርሱን ስላላወቀው ነው። [2]ወዳጆች ሆይ፤ እኛ አሁን የእግዚአብሔር ልጆች ነን፤ ወደ ፊት ምን እንደ ምንሆን ገና አልተገለጠም። እርሱ በሚገለጥበትᶜ ጊዜ እናየዋለንና፣ እርሱን እንደምን መሰል እናውቃለን። [3]በእርሱ ይህን ተስፋ የሚያደርግ ሁሉ፣ እርሱ ንጹሕ እንደ ሆነ ራሱን ያነጻል።

[4]ኀጢአት የሚያደርግ ሁሉ ዐመፅን ያደርጋል፤ ኀጢአትም ዐመፅ ነው። [5]እርሱ ኀጢአትን ሊያስወግድ እንደ ተገለጠ ታውቃላችሁ፤ በእርሱም ኀጢአት የለም። [6]በእርሱ የሚኖር ኀጢአትን አያደርግም፤ ኀጢአት የሚያደርግ ግን እርሱን አላየውም ወይም አላወቀውም። [7]ልጆች ሆይ፤ ማንም እንዳያስታችሁ ተጠንቀቁ፤ እርሱ ጻድቅ እንደ ሆነ፣ ጽድቅን የሚያደርግ ጻድቅ ነው።

ᵐ20 አንዳንድ ቅጆች፣ *እናንተ ሁሉንም ነገር ታውቃላችሁ* ይላሉ።

ᶜ2 ወይም *በሚታመቅበት ጊዜ*

2፥19 ሐሥ20፥30፤ 1ቆሮ11፥19
2፥20 ቁ27፤ኢሮ 31፥34፤ማቴ13፥11፤ ማር1፥24፤ዮሐ14፥26 ፤2ቆሮ1፥21
2፥21 2ጴጥ1፥12፤ ይሁ5
2፥22 1ዮሐ4፥3፤ 2ዮሐ7
2፥23 ዮሐ8፥19፤ 14፥7፤ 1ዮሐ4፥15፤ 5፥1፤2ዮሐ9
2፥24 ቁ7፤ዮሐ 14፥23፤15፥4፤ዮሐ 1፥3፤2ዮሐ9
2፥25 ማቴ25፥46
2፥26 1ዮሐ3፥7
2፥27 ቁ20፤ዮሐ 15፥4፤ 1ቆሮ2፥12
2፥28 ቁ1፤ኤፌ3፥12፤ቈላ3፥4፤1ተሰ2፥19፤1ዮሐ3፥2
2፥29 ዮሐ1፥13፤ 1ዮሐ3፥7
3፥1 ቁ2:10፤ዮሐ 1፥12፤3፥16፤15፥21፤ 16፥3
3፥2 ቁ1:10፤ መዝ17፥15፤ዮሐ1፥12 ፤17፥24፤ ሮሜ8፥29፤ 1ቆሮ10፥14፤ 2ቆሮ3፥18፤ቈላ3፥4፤2ጴጥ1፥4፤1ዮሐ2፥28
3፥3 መዝ18፥26፤ 2ቆሮ7፥1፤ 2ጴጥ3፥13:14
3፥4 1ዮሐ5፥17
3፥5 ቁ8፤ዮሐ3፥17 ፤2ቆሮ5፥21
3፥6 ቁ9:1ዮሐ2፥4 15፥18፤3ዮሐ11
3፥7 1ዮሐ21:6:29

ቃሚዎች፡ ከክርስቶስ ዳግም ምጽአት በፊት ብዙ የእግዚአብሔርና የሕዝቡ ጠላቶች መነሣታቸውን ተደራስያኑ እንደሚያወቁ ዮሐንስ ተገንዝቦአል። ይህም ሰው "የክርስቶስ ተቃዋሚ" (ቍ. 18)፣ "የዐመፅ ሰው" (2ተሰ2፥3)፣ እንዲሁም "አውሬው" ተብሎ አል (ራእ 13፥1-10)። ከእርሱ በፊት ግን ብዙ የክርስቶስ ተቃዋሚዎች ይመጣሉ፤ የሚለዩባቸው ባሕርያትም፦ (1) የክርስቶስን ሥጋ መሆንና ኢየሱስ መለኮት የባሕርይ ገንዘቡ የሆነ መሲሕ መሆኑን ይክዳሉ (ቍ.22፤ 4፥2፤ 2ዮሐ 7) (2) አብን ይክዳሉ (ቍ. 22) (3) አብ የላቸውም (ቍ. 23) 4) ሐሰተኞችና አታላዮች ናቸው (ቍ. 22፤ 2ዮሐ 7) (5) ብዙ ናቸው (ቍ 18) (6) ዮሐንስ በነበረበት ዘመን፣ ከአማኞች ጋር ኅብረት ስላልነበራቸው ከቤተ ክርስቲያን ራሳቸውን አግልለዋል (ቍ 19)። በዮሐንስ መልእክት ውስጥ የክርስቶስ ተቃዋሚዎች የተባሉት በለጋነት ደረጃ የነበረውን የኖስትሳውያንን ትምህርት የሚያራምዱትን ነው።

2፥20 *ከቅዱሱ፤* ኢየሱስ ክርስቶስን (ማር1፥24፤ ዮሐ6፥69፤ ሐሥ2፥27፤ 3፥14፤ 22፥14) ወይም አብን ማለት ነው። (2ነገ 19፥22፤ ኢዮ6፥10)። *ቅባት፤* መንፈስ ቅዱስን ማለት ነው። (ቍ. 27፤ ሐሥ 10፥38)።

2፥22 *ክርስቶስ ... ኢየሱስን፤* ሰው የሆነው ኢየሱስ፣ የመለኮትነት ባሕርይ ገንዘቡ የሆነ ክርስቶስ ነው (ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነውን አገላለጽ በ5፥5 ላይ ይመ፤ እንዲሁም በመግቢያው ሥር "የኖስትሳውያን ትምህርት" የሚለውን እና የ5፥6 ማብ ይመ)።

*2፥23፤* ለተመሳሳይ ሐሳብ 2ዮሐ 9 ይመ።

*2፥26፤* ይህ መልእክት ከተጻፈባቸው ዐላማዎች መካከል አንዱ ነው፡(በመግቢያው ሥር ፡- "የተጻፈበት ወቅትና ዐላማ" ይመ)።

2፥27 *ቅባት፤* የቍ. 20 ማብ ይመ። *ማንም እንዲያስተምራችሁ አያስፈልግም፤* መጽሐፍ ቅዱስ በተደጋጋሚ የትምህርትን አስፈላጊነት ስለሚናገር (ማቴ 28፥20፤ 1ቆሮ12፥28፤ ኤፌ4፥11፤ ቈላ3፥16፤ 1ጢሞ4፥11፤ 2ጢሞ2፥2:24)፣ ዮሐንስ እዚህ ላይ ሰብአዊ መምህራን አያስፈልጉም ማለቱ አይደለም። ነገር ግን መልእክቱን በሚጽፍበት ዘመን የነበሩት የኖስቲክ መምህራን፣ "ከፍተኛ ዕውቀት" ባለን በእኛ የሐዋርያት ትምህርት መታገዝ ይኖርበታል ስለሚሉ ነበር። ዮሐንስ ለእንዲህ ዐይነቱ አስተሳሰብ የሚሰጠው ምላሽ፣ ተደራሲያኑ በመንፈስ ቅዱስ አማካይነት ከሐዋርያት የተማሩት በቂ ብቻ ሳይሆን ሊደገፉት የሚገባቸው ብቸኛው ዕውነት መሆኑን ነው። *እንደሚያስተምራችሁ፤* በተለምዶ፣ "አብርሆት" የሚባለው የመንፈስ ቅዱስ የማስተማር አገልግሎት አዲስ እውነትን ወይም ለመረዳት አዳጋች የሆኑ የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍሎችን አያብራራልንም፤ ነገር ግን የተገለጠውን የእግዚአብሔር እውነት፣ በዕለት ኑሮአችን ተግባራዊ ማድረግ የምንችልበትን ዐቅም ይሰጠናል። *ስለ ሁሉም ነገር፤* ለድነትና ለክርስትና ሕይወት አስፈላጊ የሆኑትን ነገሮች ሁሉ ማለት ነው።

2፥28 *ድፍረት፤* (3፥21፤ 4፥17፤ 5፥14 ይመ)። *በእርሱ ኑሩ፤* በተማራችሁት ትምህርት ማለት ነው (ቍ. 24:27)።

2፥29 *እርሱ...ከእርሱ፤* እግዚአብሔር አብን ማለት ነው። *ጽድቅን የሚያደርግ፤* የእግዚአብሔር ቤተ ሰብ አባላት በተቀደሰ ኑሮአቸው ይታወቃሉ።

3፥1 *የእግዚአብሔር ልጆች፤* (ዮሐ1፥12 እና ማብ ይመ)።

3፥2 *እርሱ ... እርሱን፤* ክርስቶስን ማለት ነው።

3፥3 *ተስፋ፤* ተራ ምኞት ሳይሆን፣ የወደፊቱን በተመለከተ ያለውን ፍጹም እርግጠኝነት የሚያመለክት ነው (የሮሜ 5፥2 ማብ ይመ)። *እርሱ፤* ክርስቶስን ማለት ነው። *ራሱን ያነጻል፤* ከኀጢአት በመመለስ ማለት ነው።

3፥4 *ኀጢአትም ዐመፅ ነው፤* ከማንኛውም የእግዚአብሔር ትእዛዝ መራቅን የሚያመለክት ነው።

3፥6 *ኀጢአት የሚያደርግ፤* ዮሐንስ ስለ ኀጢአት አልባ ፍጽምና እየተናገረ አይደለም (1፥8-10፤ 2፥1 ይመ)፤ ነገር ግን የአማኞች ሕይወት የሚታወቀው በኀጢአት ሳይሆን ትክክለኛውን ነገር በማድረግ ነው።

8ኀጢአትን የሚያደርግ ከዲያብሎስ ነው:: ምክንያቱም ዲያብሎስ ከመጀመሪያ እንሥቶ ኀጢአትን የሚያደርግ ነው:: የእግዚአብሔር ልጅ የተገለጠውም የዲያብሎስን ሥራ ያፈርስ ዘንድ ነው:: 9ከእግዚአብሔር የተወለደ ሁሉ ኀጢአትን አያደርግም፤ የእርሱ ዘር በውስጡ ይኖራልና፤ ከእግዚአብሔር ስለ ተወለደም ኀጢአትን ሊያደርግ አይችልም:: 10የእግዚአብሔር ልጆችና የዲያብሎስ ልጆች ተለይተው የሚታወቁት በዚህ ነው:- ጽድቅን የማያደርግ፣ ወንድሙንም የማይወድ ሁሉ ከእግዚአብሔር አይደለም::

### እርስ በርሳችሁ ተዋደዱ

11ከመጀመሪያ የሰማችኋት፣ እርስ በርሳችን ልንዋደድ ይገባናል የምትለዋ መልእክት ይህች ናትና፤ 12የክፉው ወገን ሆኖ ወንድሙን እንደ ገደለው እንደ ቃየን አትሁኑ፤ ለምን ገደለው? ምክንያቱም የእርሱ ሥራ ክፉ፣ የወንድሙ ግን ጽድቅ ስለ ነበረ ነው:: 13ወንድሞች ሆይ፤ ዓለም ቢጠላችሁ አትደነቁ:: 14ወንድሞቻችንን ስለምንወድ ከሞት ወደ ሕይወት እንደ ተሻገርን እናውቃለን፤ ፍቅር የሌለው ሁሉ በሞት ይኖራል:: 15ወንድሙን የሚጠላ ነፍስ ገዳይ ነው፤ ነፍስ ገዳይም የዘላለም ሕይወት እንደሌለው ታውቃላችሁ::

16ኢየሱስ ክርስቶስ ሕይወቱን ስለ እኛ አሳልፎ ስለ ሰጠ፣ ፍቅር ምን እንደ ሆነ በዚህ እናውቃለን፤ እኛም ሕይወታችንን ስለ ወንድሞቻችን አሳልፈን ልንሰጥ ይገባናል:: 17ማንም ሀብት እያለው፣ ወንድሙ ሲቸገር አይቶ ባይራራለት፣ የእግዚአብሔር ፍቅር እንዴት በእርሱ ይኖራል? 18ልጆች ሆይ፤ በተግባርና በእውነት እንጂ በቃልና በአንደበት ብቻ እንዋደድ:: 19እኛ የእውነት ወገን መሆናችንን በዚህ እናውቃለን፤ ልባችንንም በፊቱ እናሳርፋለን፣ 20ይህም ልባችን በእኛ ላይ በሚፈርድብን ነገር ሁሉ ነው:: እግዚአብሔር ከልባችን ይልቅ ታላቅ ነውና ሁሉን ነገር ያውቃል::

21ወዳጆች ሆይ፤ ልባችን የማይፈርድብን ከሆነ በእግዚአብሔር ፊት ድፍረት አለን፤ 22ትእዛዛቱንም ስለምንጠብቅና በፊቱም ደስ የሚያሰኘውን ስለምናደርግ የምንለምነውን ሁሉ ከእርሱ እንቀበላለን:: 23ትእዛዙም በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ እንድናምንና እርሱ እንዳዘዘንም እርስ በርሳችን እንድንዋደድ ነው:: 24ትእዛዞቹንም የሚጠብቁ ሁሉ በእርሱ ይኖራሉ፤ እርሱም በእነርሱ ይኖራል:: በእኛ መኖሩን በዚህ ይኸውም እርሱ በሰጠን መንፈስ እናውቃለን::

### መናፍስትን መርምሩ

4 ወዳጆች ሆይ፤ መንፈስን ሁሉ አትመኑ፤ ነገር ግን መናፍስት ከእግዚአብሔር መሆናቸውን መርምሩ፤ ምክንያቱም ብዙ ሐሰተኞች ነቢያት ወደ ዓለም ወጥተዋልና:: 2የእግዚአብሔርን መንፈስ በዚህ ታውቃላችሁ፤ ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ እንደ መጣ

3፥8 ቍ10፤ማቴ4፥3፤ዮሐ8፥44፤ዕብ2፥14
3፥9 ቍ6፤መዝ119፥3፤ዮሐ1፥13፤1ጴጥ1፥23፤1ዮሐ5፥18
3፥10 ቍ1:2:8፤ዮሐ1፥12፤1ዮሐ2፥9፤4፥8
3፥11 ዮሐ13፥24:35፤15፥12፤1ዮሐ1፥5፤2፥7፤4፥7:11:21፤2ዮሐ5
3፥12 ዘፍ4፥8፤መዝ38፥20፤ምሳ29፥10፤ማቴ5፥37
3፥13 ዮሐ15፥18:19፤17፥14
3፥14 ዮሐ5፥24፤1ዮሐ2፥9
3፥15 ማቴ5፥21:22፤ዮሐ8፥44፤ገላ5፥20:21፤1ዮሐ2፥9፤ራእ21፥8
3፥16 ዮሐ10፥11:15፥13፤ፊል2፥17፤1ተሰ2፥8
3፥17 ዘዳ15፥7:8፤ያዕ2፥15:16፤1ዮሐ4፥20
3፥18 ሕዝ33፥31፤ሮሜ12፥9፤1ዮሐ2፥1
3፥21 1ቆሮ10፥14፤ኤፌ3፥12፤1ዮሐ5፥14
3፥22 ማቴ7፥7፤ዮሐ8፥29፤14፥15፤ዕብ13፥21
3፥23 ሉቃ24፥47፤ዮሐ1፥12፤3፥18፤6፥29፤13፥34፤20፥3 1ቆሮ6፥11፤1ዮሐ5፥13
3፥24 1ተሰ4፥8፤1ዮሐ2፥3:6፤14፥13:15
4፥1 ኤር29፥8፤ማቴ7፥15፤1ቆሮ10፥14፤12፥10፤2ተሰ2፥2፤1ዮሐ2፥18 4፥2 ዮሐ1፥14፤1ቆሮ12፥3፤1ዮሐ2፥23

3፥8 *ዲያብሎስ፡* ዮሐንስ በዚህች አጭር መልእክት ውስጥ፣ ስለ ዲያብሎስ ብዙ ይናገራል፤ (1) እዚህ ቦታ፣ "ዲያብሎስ" ተብሎአል፤ በቍ12፤ 2፥13-14፤ 5፥18-19፤ ላይ ደግሞ፣ "ክፉው" ተብሎአል:: (2) "ከመጀመሪያ እንሥቶ ኀጢአትን የሚያደርግ ነው"፤ በእግዚአብሔር ላይ መጀመሪያ ካመፀበት ጊዜ ጀምሮ፤ ማለትም አዳምና ሔዋን በኀጢአት ከመውደቃቸው በፊት ኀጢአት ያደርግ ነበር (ዮሐ 8፥44)፤ (3) መጀመሪያውኑ ሰው ኀጢአት እንዲሠራ ያደረገው እርሱ ነው፤ ኀጢአትን መሥራት የባሕርይ ገንዘባቸው ያደረጉም ሰዎች (ቍ8-12) የእርሱ ልጆች ናቸው (ቍ10) (4) እርሱ "በዓለም አለ" (4፥3)፣ ጌታን የማያምን "ዓለም በሙሉ" በእርሱ ቍጥጥር ሥር ነው (5፥19):: (5) የእግዚአብሔርን ልጆች ሊጐዳ አይችልም (5፥18)፤ 6)በተቃራኒው ግን ክርስቲያኖች እርሱን ያሸንፋሉ (2፥13-14፤ 4፥4)፤ ክርስቶስም ሥራውን ያፈርሳል::

3፥9 *የእርሱ ዘር፤* በሰው እወላለድ ሂደት ውስጥ፣ የወላጆች ሕይወትና ባሕርይ ወደሚወለደው ልጅ የሚተላለፈው፣ "በዘር" አማካይነት መሆኑን የሚያመለክት ሥዕላዊ ገለጻ ነው:: *ኀጢአትን ሊያደርግ አይችልም፤* ክርስቲያን ፈጽሞ ኀጢአት አይሠራም ማለት ሳይሆን፣ ዘወትር ኀጢአት በመሥራት አይታወቅም ማለት ነው::

3፥10 *የእግዚአብሔር ልጆችና የዲያብሎስ ልጆች፤* ይህ ዮሐንስ በ2፥28-3፥10 ባለው ክፍል ለሰጠው ትምህርት መሪና የማጠቃለያ ሐሳብ ነው:: ዐላማውም ተደራስያኑ ስለ ድኅነት የተሳሳተ ግንዛቤ እንዳይኖራቸው የሚያስጠነቅቅ ነው:: አንድ ሰው ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት ኖሮት (1፥3)፣ በኀጢአት እየተመላለሰ፣ የዲያብሎስን ሥራ እየሠራ (ቍ 8)፣ ዓለምን እየወደደ (2፥15) እንዲሁም ሌሎችን እየበደለ (ቍ14-18)፣ ድነትን ያገኘና መንግሥተ ሰማያትን ለመውረስ የሚጠባበቅ የእግዚአብሔር ልጅ መሆን ይችላል የሚለውን ማንኛውንም ዐይነት ትምህርት አማኞች እንዲቃወሙ ያበረታታል::

3፥11 *ከመጀመሪያ፤* የ2፥7 ማብ ይመ::

3፥12 *ቃየን፤* ዘፍ 4፥8፤ ዕብ 11፥4

3፥14 *ወንድሞቻችንን፤* አማኞችን ማለት ነው::

3፥15 *የሚጠላ፤* የ2፥9-10 ማብ ይመ::

*3፥17-18፤* ያዕ 2፥14-17 ይመ::

3፥17 *ወንድሙ ሲቸገር፤* አማኞች የተቸገረውን በመርዳት ፍቅራቸውን ሊያሳዩ ይገባቸዋል፤ ይህም ቍሳዊ የሆነውን ንብረታችንን ማካፈልን ይጨምራል (ዘዳ 15፥7-11):: *የእግዚአብሔር ፍቅር፤* እግዚአብሔር በአማኝ ልብ ውስጥ ያፈሰሰውንና (ሮሜ5፥5) አማኞች እርስ በርሳቸው እንዲፋቀሩ የሚያስችላቸውን፣ እግዚአብሔርም ለሰው ያለውን ዐይነት ፍቅር ማለት ነው፤ ወይም ሐረጉ፣ አማኝ ለእግዚአብሔር ያለውን ፍቅር ሊያመለክት ይችላል::

3፥22 *ትእዛዛቱንም ስለምንጠብቅና፤* ጸሎታችን ውጤት የሚኖረው ለእግዚአብሔር ባለን መሰጠት ነው፤ እግዚአብሔርን መታዘዝ፣ መውደድና ደስ ማሰኘትም በጸሎት የጠየቅነውን ነገር ለማግኘት ዐይነተኛ ነገሮች ናቸው (ዮሐ 8፥29፤ 2ቆሮ5፥9፤ ኤፌ 5፥10፤ ዕብ13፥21፤ መዝ50፥14-15፤ ምሳ15፥29፤ ኢሳ59፥1-2፤ ማቴ6፥15፤ ማር11፥25፤ ያዕ5፥16 ይመ)::

*3፥23* ይህ ትእዛዝ ሁለት ክፍሎች አሉት፤ (1) በክርስቶስ ማመን (ዮሐ 6፥29) እንዲሁም (2) እርስ በእርስ መዋደድ ናቸው (ዮሐ13፥34-35):: የመጀመሪያው ክፍል 4፥1-6፣ ሁለተኛው ደግሞ በ4፥7-12 ላይ ተብራርቶአል::

4፥1 *መንፈስን፤* ሰው በመንፈስ ቅዱስ ወይም በክፉ መንፈስ ሊመራ ይችላል:: *መናፍስት ... መርምሩ፤* ከ1ተሰ5፥2 ጋር ያነጻጽሩ:: በማቴ 7፥1 ላይ የምናገኘው እንዲህ ዐይነቱን መመርመር ሳይሆን፣ በራስ ጽድቅ በመደገፍ በሌሎች ሰዎች ግብረ ገብ ላይ መፍረድን ነው:: *ሐሰተኞች ነቢያት፤* እውነተኛ ነቢይ በመንፈስ ቅዱስ በመመራት ከእግዚአብሔር የሆነውን ብቻ ይናገራል (2ጴጥ 1፥21):: በዮሐንስ ዘመን የነበሩት ሐሰተኛ ነቢያት ግን (እንደ ኖስቲካዊ መምህራን ያሉ) የእግዚአብሔር ጠላት በሆኑ መናፍስት በመነዳት ይናገራሉ:: ክርስቶስ ከሐሰተኛ ነቢያት መጠንቀቅ እንደሚገባን አስገንዝቦናል (ማቴ 7፥15፤24፥11)፤ ጳውሎስና ጴጥሮስም እንዲሁ (1ጢሞ 4፥1፤ 2ጴጥ 2፥1)::

4፥2 *ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ እንደ መጣ፤* የ1፥1 ማብ ይመ፤ ኢየሱስ በውሃ ሲጠመቅ መሲሕነት የሆነው ክርስቶስ ገባ

የሚቀበል መንፈስ ሁሉ ከእግዚአብሔር ነው፤ [3]ኢየሱስን የማይቀበል መንፈስ ግን ከእግዚአብሔር አይደለም፤ እንደሚመጣ የሰማችሁት የክርስቶስ ተቃዋሚ መንፈስ ይህ ነው፤ አሁንም እንኳ በዓለም አለ።

[4]ልጆች ሆይ፤ እናንተ ከእግዚአብሔር ናችሁ፤ እነርሱንም አሸንፋችኋቸዋል፤ ምክንያቱም በእናንተ ውስጥ ያለው በዓለም ካለው ይበልጣል። [5]እነርሱ ከዓለም ናቸው፤ ስለዚህ የሚናገሩት እንደ ዓለም ነው፤ ዓለምም ይሰማቸዋል። [6]እኛ ከእግዚአብሔር ነን፤ እግዚአብሔርን የሚያውቅ ይሰማናል፤ ከእግዚአብሔር ያልሆነ ግን አይሰማንም፤ በዚህም የእውነትን መንፈስና የሐሰትን መንፈስ እናውቃለን።

## የእግዚአብሔር ፍቅርና የሰው ፍቅር

[7]ወዳጆች ሆይ፤ ፍቅር ከእግዚአብሔር ስለ ሆነ፣ እርስ በርሳችን እንዋደድ፤ የሚወድ ሁሉ ከእግዚአብሔር የተወለደ ነው፤ እግዚአብሔርንም ያውቃል። [8]የማይወድ ግን እግዚአብሔርን አያውቅም፤ እግዚአብሔር ፍቅር ነውና። [9]እግዚአብሔር ፍቅሩን በመካከላችን የገለጠው እንዲህ ነው፤ እኛ በእርሱ አማካይነት በሕይወት እንኖር ዘንድ እግዚአብሔር አንድያ ልጁን ወደ ዓለም ላከ። [10]ፍቅር ይህ ነው፤ እኛ እግዚአብሔርን እንደ ወደድነው ሳይሆን እርሱ እንደወደደንና ስለ ኀጢአታችን ማስተሰረያ[a] ይሆን ዘንድ ልጁን መላኩ ነው። [11]ወዳጆች ሆይ እግዚአብሔር እንዲህ ከወደደን፣ እኛም እርስ በእርሳችን መዋደድ ይገባናል። [12]እግዚአብሔርን ያየ ከቶ ማንም የለም፤ እርስ በርሳችን ብንዋደድ ግን እግዚአብሔር በእኛ ይኖራል፤ ፍቅሩም በእኛ ፍጹም ይሆናል።

[13]መንፈሱን ስለ ሰጠን፣ እኛ በእርሱ እንደምንኖር እርሱም በእኛ እንደሚኖር እናውቃለን። [14]አብ ልጁን የዓለም አዳኝ ይሆን ዘንድ እንደላከው ዐይተናል፤ እንመሰክራለንም። [15]ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ አምኖ በሚመሰክር ሁሉ፣ እግዚአብሔር በእርሱ ይኖራል፤ እርሱም በእግዚአብሔር ይኖራል። [16]ስለዚህም እግዚአብሔር ለእኛ ያለውን ፍቅር እናውቃለን፤ በፍቅሩም እናምናለን።

እግዚአብሔር ፍቅር ነው፤ በፍቅር የሚኖር በእግዚአብሔር ይኖራል፤ እግዚአብሔርም በእርሱ ይኖራል። [17]በዚህም ዓለም እርሱን እንመስላለንና። በፍርድ ቀን ድፍረት ይኖረን ዘንድ፣ ፍቅር በዚህ ዐይነት በመካከላችን ፍጹም ሆኖአል፤ [18]በፍቅር ፍርሀት የለም፤ ፍጹም ፍቅር ግን ፍርሀትን አውጥቶ ይጥላል፤ ፍርሀት ከቅጣት ጋር የተያያዘ ነውና። የሚፈራም ሰው ፍቅሩ ፍጹም አይደለም።

[19]እርሱ አስቀድሞ ወዶናልና እኛ እንወደዋለን። [20]ማንም፣ "እግዚአብሔርን እወደዋለሁ" እያለ ወንድሙን ቢጠላ፣ እርሱ ሐሰተኛ ነው፤ ያየውን ወንድሙን የማይወድ ያላየውን እግዚአብሔርን መውደድ አይችልምና። [21]እርሱም "እግዚአብሔርን የሚወድ ሁሉ ወንድሙን መውደድ ይገባዋል" የሚለውን ይህን ትእዛዝ ሰጥቶናል።

## በእግዚአብሔር ልጅ ማመን

**5** ኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ እንደ ሆነ የሚያምን ሁሉ ከእግዚአብሔር ተወልዶአል፤ አባትንም የሚወድ ሁሉ ልጁንም እንደዚሁ ይወዳል። [2]እግዚአብሔርን ስንወድና ትእዛዛቱን ስንፈጽም የእግዚአብሔርን ልጆች እንደምንወድ በዚህ እናውቃለን፤

4፥3 1ዮሐ2፥18፡22፤2ዮሐ7
4፥4 2ነገ6፥16፤ዮሐ12፥31፤16፥33፤ሮሜ8፥31፤1ዮሐ2፥1
4፥5 ዮሐ15፥19፤17፥14፡16
4፥6 ማር13፥5፤ዮሐ8፥47፤14፥17
4፥7 ዮሐ1፥13፤1ዮሐ2፥4፤3፥11
4፥8 ቍ7፡16
4፥9 ዮሐ1፥18፤3፥16፡17፤1ዮሐ5፥11
4፥10 ሮሜ3፥25፤5፥8፡10
4፥11 ዮሐ3፥16፤15፥12፤1ቆሮ10፥14፤1ዮሐ3፥11
4፥12 ቍ17፤ዮሐ1፥18፤1ዮሐ2፥5
4፥13 1ዮሐ2፥3፤3፥24
4፥14 ሉቃ2፥11፤ዮሐ3፥17፤15፥27
4፥15 1ዮሐ2፥23፤3፥24፤5፥5
4፥16 ቍ8፡12፡13፤1ዮሐ3፥24
4፥17 ቍ12፤ማቴ10፥15፤ኤፌ3፥12፤1ዮሐ2፥5
4፥18 ሮሜ8፥15
4፥19 ቍ10
4፥20 ቍ12፤ዮሐ1፥18፤1ዮሐ1፥6፤2፥4፡9፤3፥17
4፥21 ማቴ5፥43፤1ዮሐ2፥7፡9
5፥1 ዮሐ1፥13፤3፥15፤8፥42፤1ዮሐ2፥22፡23፤4፥2፡15
5፥2 1ዮሐ2፥3፤3፥14
5፥3 ማቴ11፥30፤23፥4፤ዮሐ14፥15

[a]10 *ወይም ኀጢአታችንን አስወግዶ፣ ቍጣውን ያርቅልን ዘንድ*

በት፣ በመስቀል ላይ በተሰቀለ ጊዜ ደግሞ ተለይቶት ሄደ፤ ስለዚህ በመስቀል ላይ የሞተው ሰው የሆነው ኢየሱስ ነው ብለው የሚያስተምሩትን እንደ ኖስቲሳውያን ያሉ የሐሰት መምህራንን በመቃወም ዮሐንስ ይህን ጽፎአል። *የሚቀበል፤* የአእምሮን ዕውቀት ብቻ ሳይሆን በኢየሱስ ላይ ያለንን እምነት በአደባባይ መመስከርንም ያጠቃልላል፤ ማወቅ ብቻ ከሆነ አጋንንትም ያውቃሉ፤ ይንቀጠቀጡማል (ያዕ2፥19፤ ማር 1፥24)።

4፥3 *ኢየሱስን የማይቀበል፤* በ1፥2 ላይ የተጠቀሰውን ሥጋ የሆነውን ኢየሱስ ክርስቶስን ያመለክታል (የ2፥18 ማብ ይመ)።

4፥4 *ከእግዚአብሔር፤* ከእግዚአብሔር የተወለደ ማለት ነው (2፥29፤ 3፥9-10)። *እነርሱንም፤* በክርስቶስ ተቃዋሚ መንፈስ (ቍ 3) የሚመሩትን ሐሰተኛ ነቢያት (ቍ 1) ያመለክታል። *በዓለም ካለው፤* ዲያብሎስን ማለት ነው (ዮሐ 12፥31፤ 16፥11)። በቍጥር 3 ላይ፣ "ዓለም" የሚለው ቃል ሰዎች የሚኖሩባትን ምድር ያመለክታል፤ ከቍጥር 4-5 ያለው ደግሞ የክርስቶስ ተቃዋሚዎችን ጨምሮ ከእግዚአብሔር ያልተወለዱትን ማኅበረ ሰብን ወይም ሥርዐትን ያመለክታል (ዮሐ1፥9 ማብ ይመ)።

4፥6 *የእውነትን መንፈስና፤* ከ5፥6 ጋር ያነጻጽሩ፤ ዮሐ 14፥17 ማብ ይመ።

*4፥7-5፥3፤* በዚህ መልእክት ውስጥ፣ "ፍቅር" የሚለው ቃል 42 ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን፣ በዚህ አጭር ክፍል ውስጥ ደግሞ 32 ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል።

4፥8 *እግዚአብሔርን አያውቅም፤* እግዚአብሔርን በእውነት የሚያውቁት፣ በመጠኑም እንኳ ቢሆን እርሱን የሚወዱት ብቻ ናቸው። *እግዚአብሔር ፍቅር ነውና፤* በባሕርዩና በተግባሩ ሁሉ እግዚአብሔር አፍቃሪ ነው። እግዚአብሔር መንፈስ (ዮሐ4፥24)፣ ብርሃን (1፥5)፣ ቅዱስ፣ ኀያል፣ እውነትና ጻድቅ እንደ ሆነ ዮሐንስ አስረግጦ ይናገራል።

4፥9 *አንድያ ልጁን፤* የዮሐንስ 1፥18 ማብ ይመ።

4፥10 *ስለ ኃጢአታችን ማስተሰረያ፤* የ2፥2 ማብ ይመ።

4፥12 *እግዚአብሔርን ያየ ከቶ ማንም የለም፤* የዮሐ1፥18 ማብ ይመ። እኛ ያለን ፍቅር ምንጩ የእግዚአብሔር ፍቅር ስለ ሆነ፣ ክርስቲያን ወገኖችን ስንወድ የእርሱ ፍቅር ፍጹም ይሆናል። ስለዚህ ከቶ ማንም ያላየው እግዚአብሔር፣ ወንድሞቻቸውን በሚወዱ በእነርሱ ፍቅር ይታያል፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር በእነርሱ ውስጥ ይኖራልና።

4፥16 *እግዚአብሔር ፍቅር ነው፤* የቍጥር 8 ማብ ይመ።

4፥17 *እርሱን እንመስላለንና፤* ክርስቶስን መምሰል ማለት ነው። በፍቅር በመኖር ክርስቶስን መምሰላችን፣ ፍቅር የሆነው እግዚአብሔር በእኛ ውስጥ መኖሩን ያሳያል፤ ስለዚህ ድነት ስላገኘን በፍርድ ቀን በድፍረት መቆም እንችላለን ማለት ነው።

4፥18 *በፍቅር ፍርሀት የለም፤* በፍርድ ቀን በእግዚአብሔር ፊት ፍርሀት አይኖርም፤ ምክንያቱም እውነተኛ ፍቅር የድነት ማረጋገጫ ነው።

*4፥19፤* የፍቅር ምንጭ እግዚአብሔር ስለሆነ፣ እውነተኛ ፍቅር ከሰዎች ፈቃድ ሊመነጭ አይችልም።

4፥21 *ይህን ትእዛዝ፤* ዮሐንስ 13፥34 ይመ።

5፥1 *ኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ እንደ ሆነ የሚያምን ሁሉ ከእግዚአብሔር ተወልዶአል፤* ፍቅር ዳግም የመወለድ ምልክት እንደ ሆነ ሁሉ፣ ኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ እንደ ሆነ ማመንም እንዲሁ ነው (4፥7)። *ክርስቶስ፤* የ2፥22 ማብ ይመ። *አባትን የሚወድ ሁሉ፣ ልጁንም እንዲሁ ይወዳል፤* ዮሐንስ ይህን የጻፈው፣ የቤተ ሰብ አባላት በአባት መሪነት የጠበቀ ኅብረት በነበራቸውና እንደ አንድ በሚታዩበት ዘመን ነው፤ ስለዚህ ቤተ ሰብን በምሳሌነት በመጠቀም፣ እግዚአብሔር አብን የሚወድ ሁሉ የእግዚአብሔርን ልጆች እንደሚወድ ያሳያል።

5፥2 *በዚህ እናውቃለን፤* ለሌሎች ያለን ፍቅር እውነተኛ

[3]እግዚአብሔርን መውደድ ትእዛዛቱን መፈጸም ነውና:: ትእዛዛቱም ከባድ አይደሉም፤ [4]ምክንያቱም ከእግዚአብሔር የተወለደ ሁሉ ዓለምን ያሸንፋል:: ዓለምን የሚያሸንፈውም እምነታችን ነው:: [5]ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ ከሚያምን በስተቀር ዓለምን የሚያሸንፍ ማነው?

[6]በውሃና በደም የመጣው ይህ፣ ኢየሱስ ክርስቶስ ነው:: እርሱ በውሃና በደም እንጂ በውሃ ብቻ አልመጣም:: የሚመሰክረውም መንፈስ ነው፤ መንፈስ እውነት ነውና:: [7]ስለዚህ ሦስት ምስክሮች አሉት:: [8]እነርሱም[*] መንፈሱ፣ ውሃውና ደሙ ናቸው፤ ሦስቱም ይስማማሉ:: [9]የሰውን ምስክርነት ከተቀበልን፣ የእግዚአብሔር ምስክርነት ከዚያም ይልቃል፤ ይህ ስለ ልጁ የሰጠው የእግዚአብሔር ምስክርነት ነውና:: [10]በእግዚአብሔር ልጅ የሚያምን ሁሉ በልቡ ምስክር አለው፤ ማንም እግዚአብሔርን የማያምን ሁሉ እግዚአብሔር ስለ ልጁ የሰጠውን ምስክርነት ስላላመነ ሐሰተኛ አድርጎታል:: [11]ምስክርነቱም ይህ ነው፤ እግዚአብሔር የዘላለምን ሕይወት ሰጠን፤ ይህም ሕይወት ያለው በልጁ ነው:: [12]ልጁ ያለው ሕይወት አለው፤ የእግዚአብሔር ልጅ የሌለው ሕይወት የለውም::

5፥4 ዮሐ1፥13፤ 16፥33
5፥5 ቍ1፤ 1ዮሐ2፥23
5፥6 ዮሐ14፥17፤ 19፥34
5፥7 ማቴ18፥16
5፥9 ማቴ3፥16:17፤ ዮሐ5፥32:34:37፤8፥17:18
5፥10 ዮሐ3፥33፤ ሮሜ8፥16፤ ገላ3፥6፤1ዮሐ1፥10
5፥11 ማቴ25፥46፤ ዮሐ1፥4
5፥12 ዮሐ3፥15:16:36
5፥13 ቍ11፤ ማቴ25፥46፤ 1ዮሐ3፥23
5፥14 ማቴ7፥7፤ ኤፌ3፥12፤ 1ዮሐ3፥21
5፥15 ቍ18:19:20፤ 1ነገ3፥12
5፥16 ዘፀ23፥21፤ ኤር7፥16፤ 14፥11፤ዕብ6፥4-6፤ 10፥26፤ያዕ5፥15
5፥17 ቍ16፤ ዮሐ2፥1፤3፥4
5፥18 ማቴ5፥37፤ ዮሐ1፥13፤14፥30
5፥19 ዮሐ12፥31፤ 14፥30፤17፥15፤

## ማጠቃለያ ሐሳብ

[13]በእግዚአብሔር ልጅ ስም የምታምኑ እናንተ የዘላለም ሕይወት እንዳላችሁ ታውቁ ዘንድ ይህን እጽፍላችኋለሁ፤ [14]በእግዚአብሔር ፊት ለመቅረብ ያለን ድፍረት ይህ ነው፤ ማንኛውንም ነገር እንደ ፈቃዱ ብንለምን እርሱ ይሰማናል፤ [15]የምንለምነውን ሁሉ እንደሚሰማን ካወቅን፣ የለመነውንም ነገር እንደ ተቀበልን እናውቃለን::

[16]ማንም ሰው ወንድሙ ለሞት የማያበቃ ኀጢአት ሲያደርግ ቢያየው ይጸልይ፤ እግዚአብሔርም ለሞት የማያበቃ ኀጢአት ላደረጉት ሕይወትን ይሰጣል:: ለሞት የሚያበቃም ኀጢአት አለ፤ ስለዚህኛው ግን ይጸልይ አልልም:: [17]ዐመፅ ሁሉ ኀጢአት ነው፤ ለሞት የማያበቃም ኀጢአት አለ:: [18]ከእግዚአብሔር የተወለደ ሁሉ ኀጢአት እንደማያደርግ ነገር ግን የእግዚአብሔር ልጅ እንደሚጠብቀው፣ ክፉውም እንደማይነካው እናውቃለን:: [19]እኛ ከእግዚአብሔር እንደሆንን መላው ዓለምም በክፉው ሥር እንደ ሆነ እናውቃለን::

[*]7:8 ጥንታዊ ባለሆነ በቩልጌት ቅጅ ላይ *በሰማይ የሚመሰክሩት ሦስቱ ናቸው፤ እነርሱም አብ፣ ቃልና መንፈስ ቅዱስ ናቸው* ይላል::

8. በምድር የሚመሰክሩት ሦስቱ ናቸው (ሆኖም ይህ ከ16ኛው ክፍለ ዘመን በፊት በነበሩት የግሪክ ቅጆች ውስጥ አይገኝም::

ክርስቲያናዊ ፍቅር የሚሆነው፣ እግዚአብሔርን በመውደድና ትእዛዛቱን በመጠበቅ ላይ የተመሠረተ ሲሆን ብቻ ነው (ከ2፥3፤ 3፥23፤ ዮሐ15፥10 ጋር ያነጻጽሩ፤ የዮሐ14 ፥21ማብ ይመ)::

5፥3 *ትእዛዛቱም ከባድ አይደሉም*፤ ትእዛዛቱን መጠበቅ በራሱ ቀላል ስለሆነ ሳይሆን፣ ዮሐንስ በቍ4 ላይ እንደ ገለጸው ይህ ቀላል የሚሆነው አዲሱን ልደት ከማግኘት የተነሣ ነው:: በእምነት ከእግዚአብሔር ዳግም የተወለደ ሁሉ በመንፈስ ቅዱስ ርዳታ መታዘዝ ይችላል::

5፥4 *ያሸንፋል ... የሚያሸንፈውም*፤ ዓለምን ማሸነፍ ማለት በኀጢአት በተሞላው የኑሮ ዘይቤ ላይ ድልን መቀዳጀት ማለት ነው፤ ይህም ለእግዚአብሔር መታዘዝ የተገለጠበት ሌላኛው መንገድ ነው (ቍ3):: እንዲህ ያለው መታዘዝ ለአማኝ የማያስቸግረው ዳግም ስለ ተወለደ፣ መንፈስ ቅዱስም በውስጡ ስለሚኖርና ኀይል ስለሚሰጠው ነው:: ዮሐንስ የድልን ሁለት ገጽታዎች ሲናገር:- (1) በእምነት ከዓለም ወደ እግዚአብሔር መመለስ የመጀመሪያው ድል ("የሚያሸንፈው") ሲሆን፣ (2) ክርስቲያናዊ ኑሮን በመኖር በየዕለቱ የምናገኘው ድል ሌላኛው ነው ("ያሸንፋል"):: *ዓለምን*፤ የ2፥15 ማብ ይመ::

5፥5 *የእግዚአብሔር ልጅ*፤ ይህን መሰሉን የእምነት መግለጫ በተመለከተ 2፥22፤4፥2፤ 5፥1 ይመ::

*5፥6፤* "ውሃ" የኢየሱስን መጠመቅ፣ "ደም" ደግሞ ሞቱን ያሳያል:: እነዚህ እዚህ ላይ መጠቀሳቸው፣ የኢየሱስ ምድራዊው አገልግሎት በጥምቀት ተጀምሮ በሞቱ ስለተፈጸመ ነው:: ኢየሱስ ሰው ብቻ ሆኖ እንደ ተወለደና እስከ ተጠመቀበትም ጊዜ ድረስ ሰው ብቻ ነበር እያሉ ለሚያስተምሩ፣ በዘመኑ ለነበሩት ሐሰተኛ መምህራን (ኖስቲኮች) ዮሐንስ ምላሽ ይሰጣል:: (በመግቢያው ሥር "የኖስቲሳውያን ትምህርት" የሚለውን ይመ):: ክርስቶስ (የእግዚአብሔር ልጅ) ሰው በሆነው በኢየሱስ ላይ የወረደው በጥምቀቱ ጊዜ ሲሆን፣ በመስቀል ላይ ከመሰቀሉ በፊት ግን፣ ተለይቶት ሄዶአል፤ ስለዚህ በመስቀል ላይ የሞተው ሰው ብቻ የሆነው ኢየሱስ ነው በማለት እነዚህ ሐሰተኞች ያስተምሩ ነበር:: በዚህ መልእክት ውስጥ ዮሐንስ፣ ኢየሱስ ክርስቶስ አምላክም ሰውም እንደ ሆነ በአጽንዖት ይናገራል (1፥1-4፤ 4፥2፤ 5፥5):: ፍጹም አምላክና ፍጹም ሰው የሆነው ኢየሱስ ክርስቶስ ወደ ዓለም እንደ መጣ፣ እንደ ተጠመቀና እንደ ሞተም ጽፎአል:: ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ የነበረው በጥምቀቱ ጊዜ ብቻ ሳይሆን፣ በሞቱም ጊዜ ነበር (ቍ 6):: ይህ እውነት እጅግ በጣም አስፈላጊ ነው፤ ምክንያቱም ኢየሱስ ሰው ብቻ ሆኖ ቢሞት ኖሮ፣ የሰዎችን ኀጢአት ማስተስረይ (2፥2፤ 4፥10) አይችልም ነበር:: *የሚመሰክረውም መንፈስ*፤ መንፈስ ቅዱስ፣ ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ በሁለት መንገዶች ይመሰክራል፤ (1) መንፈስ ቅዱስ ኢየሱስ ሲጠመቅ ወርዶበታል (ዮሐ1፥32-34)፤ ደግሞም (2) ኢየሱስ መጠመቁና መሞቱ እርሱ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ ያረጋግጣል ብለው ሐዋርያት የሰጡትን ምስክርነት፣ መንፈስ ቅዱስ ለአማኞች ዘወትር ይመሰክራል (2፥27፤ 1ቆሮ 12፥3)::

5፥7 *ሦስቱም*፤ የብሉይ ኪዳን ሕግ፣ "ሁለት ወይም ሦስት ምስክሮችን" ይጠይቃል (ዘዳ17፥6፤ 19፥15፤ 1ጢሞ 5፥19)::

5፥9 *የእግዚአብሔር ምስክርነት*፤ ከቍጥር 6-8 ላይ የተገለጸውን የመንፈስ ቅዱስ ምስክርነት ማለት ነው::

5፥11 *የዘላለምን ሕይወት ሰጠን*፤ አሁን ያለንን ሕይወት ማለት ነው (የዮሐ 3፥15:36 ማብ ይመ)::

5፥12 *ልጁ ያለው ሕይወት አለው*፤ ሰው ሁሉ ወንጌልን መስማት ያለበት ዘላለማዊ ሕይወት የሚገኘው በእግዚአብሔር ልጅ ስለ ሆነና ከዚህም ውጭ ሕይወትን ማግኘት የሚቻልበት ሌላ መንገድ ስለሌለ ነው (ዮሐ 14፥6)::

*5፥13፤* ይህ መልእክቱ የተጻፈበት ሌላው ዐላማ ነው (2፥26 ይመ):: በመግቢያው ሥር "ዐላማው" የሚለውን ይመ::

5፥14 *ማንኛውንም ነገር እንደ ፈቃዱ ብንለምን*፤ ጸሎትን አስመልክቶ የሚያስፈልጉንን ሌሎች መመሪያዎች በተመለከተ 3፥21-22 ይመ::

*5፥16፤* ቍጥር 16 እና 17 እግዚአብሔር የሚመልሰውን የልመና ዐይነትን ያብራራል (ቍ 14-15):: *ለሞት የሚያበቃም ኀጢአት*፤ በዚህ ዐውድ መሠረት ይህ አባባል የሚያመለክተው፣ የክርስቶስን ሥጋ መሆንና የግብረ ገብን ግዴታ የሚክዱትን ኖስቲኮችን ነው፤ ይህ ኀጢአት ለሞት የሚያበቃ የተባለበት ምክንያት፣ እውነትን ሆን ብሉ በመካድ አስነዋሪ ሕይወትን መኖር ገንዘብ ስላደረጉት ነው:: ንስሓ ያልተገባበት እንዲህ ዐይነቱ ኀጢአት መንፈሳዊን ሞት ያስከትላል:: አንዳንዶች ደግሞ ክፍሉ ስለ ሥጋዊ ሞት የሚናገር ነው ይላሉ፤ ይኸውም አማኝ ኀጢአትን ሲያዘወትር እግዚአብሔር በሞት ይቀጣዋል (1ቆሮ11፥30):: ሁለቱም አመለካከቶች (ሁኔታዎች) "ለሞት የሚያበቃ ኀጢአት" የተባለው በባሕርይው ቀለል ያለ እንደ ሆነ ይስማማሉ::

*5፥18-20፤* በዚህ መልእክት ማጠቃለያ ላይ "እናውቃለን" የሚለው ቃል ሦስት ግዜ ተጠቅሷል፤ ይህም የመልእክቱን ዐበይት ሐሳቦች የሚያጠቃልል ነው::

5፥18 *የእግዚአብሔር ልጅ*፤ ኢየሱስ ክርስቶስን ማለት ነው::

[20]የእግዚአብሔር ልጅ እንደ መጣ፤ እውነተኛ የሆነውን እርሱን እንድናውቅ ማስተዋልን እንደ ሰጠን እናውቃለን፤ እኛም እውነተኛ በሆነው በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ አለን። እርሱ እውነተኛ አምላክና የዘላለም ሕይወት ነው።

[21]ልጆች ሆይ፤ ራሳችሁን ከጣዖቶች ጠብቁ።

1ዮሐ4፥6
5፥20 ቆላ5፡11፤ ማቴ25፥46፤ሉቃ24፥45፤ዮሐ17፥3
5፥21 1ቆሮ10፥14፤ 1ተሰ1፥9፤1ዮሐ2፥1

5፥20 *እውነተኛ የሆነውን እርሱን፤* እግዚአብሔር አብን ማለት ነው። *እርሱ እውነተኛ አምላክና፤* እግዚአብሔር አብን ወይም እግዚአብሔር ወልድን ሊያመለክት ይችላል። *የዘላለም ሕይወት፤* ይህ መልእክት በዚህ መሪ ሐሳብ ጀምሮ በዚሁ ሐሳብ ይደመድማል (1፥1-2)።

# የሐዋርያው ዮሐንስ መልእክት – ሁለተኛ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

የመልእክቱ ጸሐፊ ሐዋርያው ዮሐንስ ነው። በ1ኛ ዮሐንስና በዮሐንስ ወንጌል መካከል ያለው ተመሳሳይነት ይህኛውን ጨምሮ፣ ሦስቱንም የጻፋቸው አንድ ሰው መሆኑን ያመለክታል። የሚከተሉትን ያነጻጽሩ።

| 2ኛ ዮሐንስ | 1ኛ ዮሐንስ | የዮሐንስ ወንጌል |
|---|---|---|
| ቊ5 | 2፥7 | 13፥34-35 |
| ቊ6 | 5፥3 | 14፥23 |
| ቊ7 | 4፥2-3 | ----- |
| ቊ12 | 1፥4 | 15፥11፤16፥24 |

በ1ኛ ዮሐንስና በዮሐንስ ወንጌል መግቢያ በሚለው ሥር "ጸሓፊው" የሚለውን ይመልከቱ።

### መልእክቱን የተጻፈበት ጊዜ

ከዚህ በላይ ያሉት ጥቅሶች እንደሚጠቁሙት ይህ መልእክት የተጻፈው 1ኛ ዮሐንስ በተጻፈበት ጊዜ (85-95 ዓ.ም) ሳይሆን አይቀርም (በ1ኛ ዮሐንስ መግቢያ ሥር "መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ)።

### ዐላማው

በመጀመሪያዎቹ ሁለት ምእተ ዓመታት፣ ከቦታ ወደ ቦታ በመዘዋወር የሚያገለግሉ ወንጌላውያንና መምህራን የወንጌልን መልእክት ወደ ተለያዩ ቦታዎች ያደርሱ ነበር። አማኞችም እንደ ተለመደው እነዚሁኑ የወንጌል መልእክተኞች ወደ ቤታቸው ወስደው ማረፊያ ይሆኗቸው፣ ያስተናግዷቸውና በመጨረሻም የመንገድ ስንቅ ሰጥተው ይሸኟቸው ነበር። የኖስቲስ አስተማሪዎችም እኛስ ለምን ይቅርብን በማለት እንደ እውነተኞቹ ወንጌላውያንና መምህራን ያደርጉ ስለ ነበር (የ3ዮሐ ቊ5 ማብ ይመ)፣ ምእመናን (አማኞች) ተቀብለው የሚያስተናግዷቸው መምህራን እነማን መሆናቸውን ለይተው ያውቁ ዘንድ እንዲረዳቸው 2ኛው የዮሐንስ መልእክት ተጽፎላቸዋል። አለበለዚያ ካለማወቅ የተነሣ ለስሕተት ትምህርቱ መስፋፋት እስተዋፅኦ ሲያደርጉ ሊገኙ ይችላሉ።

### አስተዋፅኦ

1) ሰላምታ (1-3)
2) ምስጋና (4)
3) ምክርና ማስጠንቀቂያ (5-11)
4) መደምደሚያ (12-13)

[1]ሽማግሌው፤

በእውነት ለምወዳት እኔ ብቻ ሳልሆን እውነትን የሚያውቁ ሁሉ ለሚወዷት ለተመረጠችው እመቤትና ለልጆቿ፤ [2]በውስጣችን ከሚኖርና ከእኛ ጋር ለዘላለም ከሚሆን እውነት የተነሣ፣ [3]ከእግዚአብሔር አብና የአብ ልጅ ከሆነው ከኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ፣ ምሕረትና ሰላም በእውነትና በፍቅር ከእኛ ጋር ይሆናል።

[4]ከልጆችሽ አንዳንዶቹ ከአብ በተሰጠን ትእዛዝ መሠረት በእውነት ጸንተው እየሄዱ በማግኘቴ እጅግ ደስ ብሎኛል። [5]አሁንም እመቤት ሆይ፤ ከመጀመሪያ የነበረችውን እንጂ አዲስ ትእዛዝ አልጽፍልሽም፤ ይኸውም እርስ በርሳችን እንዋደድ ዘንድ ነው። [6]ይህም ፍቅር፤ በትእዛዙ መሠረት እንመላለስ ዘንድ ነው። ትእዛዙም ከመጀመሪያ እንደ ሰማችሁት በፍቅር እንድትኖሩ ነው።

[7]ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ እንደ መጣ የማያምኑ ብዙ አሳቾች ወደ ዓለም ወጥተዋል። እንዲህ ያለ ማንኛውም ሰው አሳሳችና የክርስቶስ ተቃዋሚ ነው። [8]እናንተም የደከማችሁበትን ዋጋ እንዳታጡ፣ ነገር ግን ሙሉ ሽልማት እንድትቀበሉ ለራሳችሁ ተጠንቀቁ። [9]በክርስቶስ ትምህርት የማይኖርና ከትምህርቱ ስቶ የሚወጣ ሁሉ አምላክ የለውም፤ በክርስቶስ ትምህርት የሚኖር ግን አብም ወልድም አለው። [10]ማንም ወደ እናንተ ቢመጣ፣ ይህንንም ትምህርት ባያመጣ በቤታችሁ አትቀበሉት፤ ሰላምም አትበሉት፤ [11]የሚቀበለው ሰው የክፉ ሥራው ተባባሪ ይሆናልና።

[12]የምጽፍላችሁ ብዙ ነገር ነበረኝ፤ ይሁን እንጂ በወረቀትና በቀለም እንዲሆን አልፈልግም፤ ዳሩ ግን ደስታችን ፍጹም ይሆን ዘንድ ወደ እናንተ መጥቼ ፊት ለፊት ላነጋግራችሁ ተስፋ አደርጋለሁ።

[13]የተመረጠችው የእኅትሽ ልጆች ሰላምታ ያቀርቡልሻል።

1፥1 ቍ3፡13፤ ዮሐ 8፥32፤ሐሥ11፥30፤ ሮሜ16፥13፤1ጢሞ 2፥4፤1ጴጥ5፥13፤ 3ዮሐ1
1፥2 ዮሐ14፥17፤ 2ጴጥ1፥12፤1ዮሐ1፥8
1፥3 ሮሜ1፥7
1፥4 ዮሐ3፥4
1፥5 1ዮሐ2፥7
1፥6 ዮሐ14፥15፤ 1ዮሐ2፥5:7
1፥7 ዮሐ1፥14፤ 1ዮሐ2፥18:22፤ 4፥1:2:3
1፥8 ማቴ10፥42፤ማር 10፥29:30፤1ቆሮ3፥8 ፤ዕብ10፥35:36፤ 11፥26
1፥9 ዮሐ8፥31፤ 1ዮሐ2፥23
1፥10 ሮሜ16፥17
1፥11 1ጢሞ5፥22
1፥12 ዮሐ3፥29፤ 3ዮሐ13:14
1፥13 ቍ1

1 *ሽማግሌው*፤ የ1ጢሞ3፥1 ማብ ይመ። ዮሐንስ በሕይወቱ መጨረሻ አካባቢ፣ በሽምግልና አገልግሎአል፤ ምናልባት ያገለገለው በኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን ሊሆን ይችላል። ሐዋርያው ጴጥሮስም ተመሳሳይ አገልግሎት ነበረው (1ጴጥ 5፥1)። *እውነትን*፤ የዮሐንስ 1፥14 ማብ ይመ። *ለተመረጠችው እመቤትና*፤ ይህ በስም የማትታወቅን በእስያ የምትኖር አንዲት ክርስቲያንን የሚያመለክት ወይም በተለዋጭ ዘይቤ በዚያ የምትገኘውን አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን የሚያሳይ ሊሆን ይችላል። *ለልጆቿ*፤ የዚያች ክርስቲያን ሴት ልጆች ወይም የዚያች አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን አባላትን ሊያመለክት ይችላል።

3 *ጸጋ … ሰላም*፤ የገላ 1፥3፤ የኤፌ 1፥2 ማብ ይመ። *ምሕረት*፤ የሮሜ 9፥23 ማብ ይመ።

4 *በእውነት ጸንተው እየሄዱ*፤ ሕይወታቸውን በእግዚአብሔር ቃል እየመሩ ማለት ነው።

5 *አዲስ ትእዛዝ*፤ የ1ዮሐ2፥7 ማብ ይመ

6 *ከመጀመሪያ*፤ የ1ዮሐ 2፥7 ማብ ይመ።

*7-11*፤ ይህ ክፍል፣ "የእግዚአብሔር ልጅ ሥጋ አልሆነም (ዮሐ1፥14)፤ ነገር ግን በኢየሱስ ጥምቀትና ስቅለት መካከል ባሉት ጊዜያት፣ በጊዜያዊነት ብቻ በኢየሱስ ላይ ኖሮበታል የሚለውንና በ1ዮሐንስ ላይ በሰፊው የተወገዘውን የኑፋቄ ትምህርት በመቃወም የተጻፈ ነው (በ1ዮሐንስ መግቢያ ሥር፣ "የኖስቲሳውያን ትምህርት" የሚለውን ይመ 1፥14)።

7 *ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ እንደ መጣ* የ1ዮሐ 4፥2-3 እና ማብ ይመ። *የክርስቶስ ተቃዋሚ*፤ የ1ዮሐ 2፥18 ማብ ይመ።

8 *የደከማችሁበትን … ሽልማት*፤ በምድር ላይ በታማኝነት የተሠራ ሥራ፣ ወደ ፊት ሽልማትን ያስገኛል (ማር 9፥41፤ 10፥29-30፤ ሉቃ 19፥16-19፤ ዕብ 11፥26 ይመ)።

9 *በክርስቶስ ትምህርት*፤ ይህ መልእክት ከ1ዮሐንስ ጋር ተመሳሳይ መሆኑ፣ የሚቃወመው የኑፋቄ ትምህርት አንድ ዐይነት መሆኑና ክፍሉ የሚገኝበት ዐውድ እንደሚጠቁመው፣ ሐረጉ ክርስቶስ ያስተማረውን ትምህርት ሳይሆን፣ ክርስቶስ ፍጹም አምላክና ፍጹም ሰው ስለ መሆኑ የተሰጠውን ትምህርት የሚያመለክት ነው። *የሚወጣ*፤ ከሐዋርያት ትምህርት ልቀው የሄዱ የሚመስላቸውን የኖስቲክ መምህራንን ያመለክታል። *አምላክ የለውም*፤ በክርስቶስና በሐዋርያቱ የተገለጠውን እውነት ለማይቀበሉ ሁሉ እግዚአብሔር አብ አምላካቸው አይደለም።

10 *በቤታችሁ አትቀበሉት*፤ ተጓዥ መምህራንን በቤት መቀበልንና መመገብን ይመለከታል (መግቢያውን ይመ)። ይህ ትእዛዝ፣ ከመናፍቃን ጋር ሰላምታ መለዋወጥንና እነርሱን ለማነጋገር ወደ ቤት ማምጣትን የሚከለክል አይደለም። ዮሐንስ የሚያስጠነቅቀው መጠለያ፣ ምግብ መስጠትና በገንዘብ መርዳትን ነው፤ ምክንያቱም ይህን ማድረግ የሐሰት መምህራንን፣ "በክፉ ሥራቸው" መተባበር፣ በሕዝቡም ዘንድ ተቀባይነት እንዲኖራቸው ማድረግ ነው (ቍ 11)።

12 *በወረቀትና በቀለም*፤ ወረቀት የሚሠራው ከፓፒረስ ሲሆን፣ በቀላሉ የሚገኝና ርካሽ ነው። "ቀለም" የሚለው ቃል በግሪኩ ጥቍር ቀለምን የሚያሳይ ሊሆን፣ የሚሠራውም ከስልን፣ ውሃንና ሙጫን በማደባለቅ ነው። *ደስታችን ፍጹም ይሆን ዘንድ*፤ 1ዮሐ 1፥4 ይመ።

13 *የተመረጠችው የእኅትሽ* ቃሉ አንዲት ሌላ ክርስቲያንን ወይም በተለዋጭ ዘይቤ ሌላ አጥቢያ ቤተክርስቲያን የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (የቍ 1ማብ ይመ)።

# የሐዋርያው ዮሐንስ መልእክት – ሦስተኛ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

የመልእክቱ ጸሐፊ ሐዋርያው ዮሐንስ ነው:: ጸሐፊው በ2ኛውና በ3ኛው መልእክታቱ የመጀመሪያ ቍጥሮች ላይ ራሱን "ሽማግሌው" ሲል እናገኘዋለን:: በሁለቱም መልእክታት፣ ሌሎች ተመሳሳይ ነገሮች አሉ፤ "በእውነት ለምወደው(ዳት)" (የሁለቱም መልእክቶች የመጀመሪያ ቍጥር)፣ "በእውነት የሚሄዱ የሚመላለሱ"(የሁለቱም መልእክቶች ቍ.4) እና ተመሳሳይ መደምደሚያቸውንም መጥቀስ ይቻላል:: በዮሐንስ መልእክት አንደኛና በዮሐንስ ወንጌል፣ "መግቢያ" በሚለው ሥር፣ "ጸሐፊው" የሚለውን ይመ::

### መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ

ይህ መልእክት የተጻፈው፣ 1ኛና 2ኛ መልእክቱ በተጻፉበት ጊዜ (85-95 ዓ.ም) ሳይሆን አይቀርም:: በ1ኛ ዮሐንስ መግቢያ ሥር "መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ)::

### ዐላማው

በዮሐንስ መልእክት ሁለተኛው መግቢያ ሥር፣ "ዐላማው" የሚለውን ይመ:: በዮሐንስ የተላኩት ተዘዋዋሪ የወንጌል መልእክተኞች፣ በእስያ ከሚገኙት አቢያተ ክርስቲያናት የአንዱ እምባገነን መሪ በነበረው በዲዮጥራጢስ ተቃውሞ ደርሶባቸው ነበር:: ዲዮጥራጢስ የዮሐንስን መልእክተኞች የሚያስተናግዱትን እንኳ ሳይቀር ከቤተ ክርስቲያን አባልነት ይሠርዛቸው ነበር:: ስለዚህ ዮሐንስ ለወንጌል መልእክተኞቹ ድጋፍ ያደረገውን ጋይዮስን ለማመስገንና ዲዮጥራጢስን ለማስጠንቀቅ ይህን መልእክት ጽፎ ልኮአል::

### አስተዋፅኦ

1) ሰላምታ (1-2)
2) ለጋይዮስ የተጻፈ ምስጋና (3-8)
3) ዲዮጥራጢስን ማውገዝ (9-10)
4) ለጋይዮስ የተላከ ምክር (11)
5) የድሜጥሮስ ምሳሌነት (12)
6) መደምደሚያ (13-14)

[1]ሽማግሌው፤

በእውነት ለምወደው ለውድ ወዳጄ፣ ለጋይዮስ፤

[2]ወዳጅ ሆይ፤ ነፍስህ በመልካም ሁኔታ ላይ እንዳለች ሁሉ መልካም ጤንነት እን ዲኖርህና በነገር ሁሉ እንዲሳካልህ እጸል ያለሁ። [3]ለእውነት ታማኝ እንደ ሆንህና የምትመላለስውም በእውነት እንደ ሆነ እን ዳንድ ወንድሞች መጥተው ስለ አንተ ሲመሰክሩ ልኝ እጅግ ደስ አለኝ። [4]ልጆቼ በእውነት የሚመላለሱ መሆናቸውን ከመስማት የሚበ ልጥ ደስታ የለኝም።

[5]ወዳጅ ሆይ፤ ለአንተ እንግዶች ቢሆ ኑም እንኳ ለወንድሞች በምታደርገው ነገር ሁሉ ታማኝ ነህ። [6]እነርሱ አንተ ስላለህ ፍቅር በቤተ ክርስቲያን ፊት መስክረዋል፤ በመንገ ዳቸውም እግዚአብሔርን ደስ በሚያሰኝ ሁኔታ ብትረዳቸው መልካም ታደርጋለህ፤ [7]ስለ ስሙ የወጡት ከአሕዛብ ምንም ሳይቀበሉ ነውና። [8]እንግዲህ አብረን ለእውነት እንድንሠራ እንዲህ ያሉትን ሰዎች ልናስተናግድ ይገባናል።

1፥1 ሐሥ11፥30፤ 2ዮሐ1
1፥3 ቆላ5:10፤ ሐሥ1፥16፤2ዮሐ4
1፥4 ቆላ3:1ዮሐ2፥1
1፥5 ቆላ31 ሮሜ12፥13፤ዕብ13፥2
1፥6 1ቆሮ16፥11፤ 2ቆሮ1፥16፤ኤፌ4፥1
1፥7 ዮሐ15፥21፤ ሐሥ20፥33:35
1፥10 ቆላ5:14፤ ዮሐ9፥22:34፤ 2ዮሐ12
1፥11 መዝ34፥14፤ 37፥27፤1ዮሐ2፥29፤ 3፥6:9:10
1፥12 ዮሐ19፥35፤ 21፥24፤1ጢሞ3፥7
1፥14 ዮሐ10፥31 ሮሜ1፥7፤ኤፌ6፥23፤ 2ዮሐ12

[9]ለቤተ ክርስቲያኒቱ ጽፌ ነበር፤ ነገር ግን መሪ መሆን የሚወደው ዲዮጥራጢስ አይቀ በለንም። [10]ስለዚህ እኔ ከመጣሁ እርሱ በክፉ ቃላት ስማችንን ለማጥፋት የሚያደርገውን ሁሉ ይፋ አወጣለሁ፤ ይህም አልበቃ ብሎት ወንድሞችን አይቀበልም፤ ሊቀበሏቸው የሚፈልጉትን ይከ ለክላቸዋል፤ ከቤተ ክርስቲያንም ያስወጣቸዋል።

[11]ወዳጅ ሆይ፤ መልካም የሆነውን እንጂ ክፉውን አትምሰል። መልካም የሆነውን የሚያ ደርግ ሁሉ ከእግዚአብሔር ነው። ክፉ የሚያ ደርግ ግን እግዚአብሔርን አላየውም። [12]ለድሜ ጥሮስ፣ ሰው ሁሉ ይመሰክርለታል፤ እውነት ራሷም ትመሰክርለታለች፤ እኛ ደግሞ እንመሰ ክርለታለን፤ እናንተም ምስክርነታችን እውነት እንደ ሆነ ታውቃላችሁ። [13]የምጽፍልህ ብዙ ነገር ነበረኝ፤ ይሁን እንጂ በቀለምና በብርዕ እንዲሆን አልፈልግም፤ [14]በቅርቡ ላይህ ተስፋ አደርጋለሁ፤ ፊት ለፊትም እንነጋገራለን። [15]ሰላም ለአንተ ይሁን፤ ወዳጆች ሰላምታ ያቀ ርቡልሃል። ለወዳጆች በየስማቸው ሰላምታ አቅርብልኝ።

1 *ሽማግሌው፤* የ2 ዮሐ 1 ማብ ይመ። *በእውነት፤* የዮሐ 1፥14 ማብ ይመ። *ውድ ወዳጄ፤* ለዮሐንስ የተወደደ አባል ነው (የዮሐ 2፥7 ማብ ይመ)። *ለጋይዮስ፤* በእስያ ከሚገኙ አብያተ ክርስቲያናት በአንዱ የሚገኝ ክርስቲያን ነው። ጋይዮስ የሚለው ስም፣ ብዙ ሮማውያን የሚጠሩበት ስም ነው።

2 *መልካም ጤንነት፤* የሥጋ ጤንነትን ያመለክታል፤ ምናል ባትም ጋይዮስ ታሞ እንደ ነበረ ሊያሳይ ይችላል።

4 *ልጆቼ፤* ምናልባት ዮሐንስ ወንጌል ሰብኮላቸው የተለወጡ ትን ወይም በዚያን ጊዜ ከእርሱ መንፈሳዊ ትምህርት ተጠቃሚ የሆኑትን አማኞች ያመለክታል።

5 *ለወንድሞች በምታደርገው፤* የቀደመችው ቤተ ክርስቲ ያን የወንጌል መልእክተኞችን በመቀበል እስፈላጊውን እገዛ ታደ ርግ ነበር (የ2ዮሐ 10 ማብ ይመ)፤ እንዲሁም የ2 ዮሐንስ መግቢያ ይመ።

6 *በመንገዳቸውም...ብትረዳቸው፤* በጉዞአቸው ምግብ፣ ገንዘብና ለመጓጓዣ የሚሆን ነገር በማዘጋጀት መርዳትን ያመለክታል።

7 *ስሙ፤* የሐሥ 4፥12 ማብ ይመ። ዛሬም አጥባቂ አይሁ ዳውያን እግዚአብሔርን የሚጠሩት "ሐ - ሼም" (ስሙ) በሚል መጠሪያ ነው።

9 *ለቤተ ክርስቲያኒቱ፤* አንዳንዶች ይህችን ቤተ ክርስቲያን በ2 ዮሐንስ 1 ላይ የተጠቀሰችው ሴት ናት ይላሉ። *ጽፌ ነበር፤* ቤሐዋርያው ተጽፎ የነበረና በኋላ ግን የጠፋ ደብዳቤ ሊሆን ይችላል። *ዲዮጥራጢስ፤* ቤተክርስቲያንን የሚመራ ጎናና መሪ ነው። ሰዎችን ከቤተ ክርስቲያን ኅብረት የሚያባርር መሆኑ (ቁ10)፣ በቤተ ክርስቲያኒቱ ውስጥ ከፍተኛ ተሰሚነት እንደ ነበረው ያሳያል።

11 *መልካም የሆነውን የሚያደርግ፤* ያለ ማቋረጥ የሚደረገ ውን መልካም ተግባር እንጂ፣ አልፎ አልፎ የሚደረገውን አያመለ ክትም።

*13-14፤* ከእዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነውን ማጠቃለያ በ2ዮሐ 12-13 ላይ ይመ።

15 *ሰላም ለአንተ ይሁን፤* ይህ ሐረግ ጸሎት ወይም ምኞት ሳይሆን ቡራኬ ነው (የዮሐ14፥27፤ 20፥19፤ ገላ 1፥3፤ ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ)።

# የያዕቆብ ወንድም የይሁዳ መልእክት

## መግቢያ

### ጸሐፊው

የመልእክቱ ጸሐፊ ራሱን ይሁዳ በማለት ገልጾአል (ቍ1)፤ በዕብራይስጡ "ዩዳህ"፣ በግሪኩ "ዩዳስ" ተብሎአል:: ይህ ስም በአይሁድ ዘንድ የተለመደ ስም ነው:: በአዲስ ኪዳን በዚህ ስም ከተጠሩት ሰዎች መካከል የዚህ መልእክት ጸሐፊዎች ሊሆኑ እንደሚችሉ የተገመቱት፣ (1) ሐዋርያው ይሁዳ (ሉቃ 6፥16፤ ሐሥ 1፥13፤ የአስቆርቱ ይሁዳ አይደለም):: (2) የጌታ ወንድም የነበረው ይሁዳ (ማቴ 13፥55፤ ማር 6፥3) በተለይም ይኸኛው ይሁዳ የዚህ መልእክት ጸሐፊ ሊሆን እንደሚችል ይታመናል:: ጸሐፊው ሐዋርያ መሆኑን አልተናገረም፤ እንዲያውም ከሌሎች ሐዋርያት ራሱን የሚለይ ይመስላል (ቍ17):: ከዚያም በላይ ጸሐፊው ራሱን የያዕቆብ ወንድም በማለት ገልጾአል (ቍ1):: ይሁዳ በኖረበት ዘመን የሚኖር ማንኛውም ሰው የማን ልጅ እንደ ሆነ እንጂ የማን ወንድም እንደ ሆነ መግለጽ የተለመደ አልነበረም:: የይሁዳ አቀራረብ ልዩ የሆነበት ምክንያት ያዕቆብ በኢየሩሳሌም ቤተ ክርስቲያን ታዋቂ ሰው ስለ ነበር ሳይሆን አይቀርም (ከያዕቆብ መልእክት "ጸሐፊው" የሚለውን ይመ)::

ይሁዳም ሆነ ያዕቆብ የጌታ ወንድሞች መሆናቸውን ባይገልጹም፣ ሌሎች ቅዱሳን ግን ይህን እውነት ለመግለጥ አላመነቱም (ማቴ 13፥55፤ ዮሐ 7፥3-10፤ ሐሥ 1፥14፤ 1ቆሮ 9፥5፤ ገላ 1፥19 ይመ):: የዮሴፍና የማርያም ቤተ ሰብ አባላት ከመሆናቸው የተነሣ የተለየ ክብር ስለ ነበራቸው ምንም ዐይነት ጥያቄ አላነሡም::

### መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ

ይህ መልእክት የጌታ ወንድም የነበረው ይሁዳ ከኖረበት ዘመን በኋላ ተጽፎአል የሚያሰኝ ምንም ዐይነት ማስረጃ የለም:: ጸሐፊው የሚቃወመው ኑፋቄ በሁለተኛው ምእተ ዓመት የነበረውን የሐሰት ትምህርት ዐይነት ሳይሆን፣ በ2ኛው የጴጥሮስ መልእክት እንደ ተጻፈው በጥንታዊቷ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ቀደም ብሎ ያደገና የተስፋፋ ትምህርት ነበር (ከሐሥ 20፥29-30፤ ሮሜ 6፥1፤ 1ቆሮ 5፥1-11፤ 2ቆሮ 12፥21፤ ገላ 5፥13፤ ኤፌ 5፥3-17፤ 1ኛ ተሰ 4፥6 ጋር ያነጻጽሩ፤ ከ2ኛ ጴጥሮስ መግቢያ "የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ):: በተጨማሪም አንዳንዶች እንደሚሉት ይህ መልእክት ከሐዋርያት ዘመን በኋላ መጻፉን የሚያመለክት ምንም ዐይነት ፍንጭ በመልእክቱ ውስጥ አይገኝም፤ የይሁዳ መልእክት ተደራሲያን ከሐዋርያት መካከል የአንዳንዶቹን ንግግር ሳይሰሙ አልቀሩም (ቍ 17-18 ይመ):: እንደዚሁም ቍ 3 ላይ "እምነት" የሚለው ቃል የታመነውን እውነት የሚያመለክት ሆኖ በጥቅም ላይ መዋሉ መልእክቱ ዘግይቶ መጻፉን አያመለክትም:: በገላትያ 1፥23 ላይ ቀደም ሲል ከተጠቀሰው ቃል ጋር ተመሳሳይ ነው:: በይሁዳና በ2ኛ ጴጥሮስ መልእክታት መካከል ዝምድና መኖሩ በተመሳሳይ ጊዜ መጻፋቸውን ያመለክታል:: 2ኛ ጴጥሮስ የይሁዳን መልእክት ተጠቅሞ ከሆነ (ከ2ኛ ጴጥሮስ መግቢያ "2ኛ ጴጥሮስና የይሁዳ መልእክት" የሚለውን ይመ) የይሁዳ መልእክት ከ2ኛ ጴጥሮስ በፊት ማለትም በ65 ዓ.ም. አካባቢ መጻፍ ነበረበት:: አለበለዚያ በ80 ዓ.ም. አካባቢ ተጽፎ ይሆናል::

### ተደራሲያኑ

ይሁዳ መልእክቱን የጻፈላቸው ሰዎች እነማን እንደ ሆኑ በግልጽ የተጠቀሰ ነገር የለም (ቍ1 ይመ):: ምናልባት ከአይሁድ ወገን ክርስትናን ለተቀበሉ ወይም ከአሕዛብ ወገን ለሆኑ ወይም ደግሞ ለሁለቱም ሊሆን ይችላል:: የት እንደሚኖሩም አልተገለጸም:: 2ጴጥሮስ ም2 እና ይሁዳ 4-18 ተመሳሳይ ሁኔታዎችን በመግለጻቸው ብቻ የሁለቱም መልእክት ተደራሲያን አንድ ናቸው ማለት አይቻልም:: ከላይ በተጠቀሱት ሁለት ምንባቦች የተገለጹት የሐሰት ትምህርቶች በአዲስ ኪዳን ዘመን ተሠራጭተው ነበር ("መልእክክቱ የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ)::

### የተጻፈበት ዐላማና ሁኔታ

ይሁዳ ለተደራስያኑ ስለ ድነት የመጻፍ ጕጕት በነበረው ጊዜ የእግዚአብሔርን ጸጋ አጥላልተው የሚያስተምሩና (ቍ 4) ሥነ ምግባር የጐደላቸው አንዳንድ የሐሰት መምህራን ተነሥተው ነበር፤ እነርሱን በቅድሚያ ማስጠንቀቅ እንደሚገባው በማሰብ ይህን መልእክት ጽፎላቸዋል:: እነዚህ ሐሰተኛ መምህራን አማኞች በጸጋ ከዳኑ በኋላ ኀጢአታቸው እንደማይቈጠርባቸውና ኀጢአት የመሥራትም ፈቃድ የተሰጣቸው እንደ ሆነ ለማሳመን ጥረት አድርገዋል:: ይሁዳ ተደራሲያኑን፣ ከእንዲህ ዐይነት ሰዎች እንዲጠነቀቁና የተጣመመውን ትምህርታቸውን በሚያድነው የእግዚአብሔር ጸጋና የእውነት ትምህርት ለመቃወም መዘጋጀት እንዳለባቸው ሊያሳስባቸው ፈልጎአል::

እነዚህ ሐሰተኛ መምህራን ኖስቲኮች እንደ ሆኑ ይገመታል:: ግምቱ ትክክል ከሆነ ሳደገው የ2ኛው ምእተ ዓመት የኖስትውያን አስተምህሮ መሥራቾች መሆናቸውም ግልጽ ነው (ከ2ኛ ጴጥሮስ መግቢያ "የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን ይመ)::

**አስተዋፅኦ**

1. ሰላምታ (1-2)
2. የመልእክቱ ወቅታዊ ሁኔታ (3-4)
   ሀ. የመልእክቱ ርእስ ጉዳይ መለወጥ (3)
   ለ. ርእስ ጉዳዩ የተለወጠበት ምክንያት (4)
3. ስለ ሐሰተኞች መምህራን የተሰጠ ማስጠንቀቂያ (5-16)
   ሀ. ስለ ተፈረደባቸው ክሓዲዎች ታሪካዊ ምሳሌዎች
      (1) እምነት የጐደላት እስራኤል (5)
      (2) የወደቁ መላእክት (6)
      (3) ሰዶምና ገሞራ (7)
   ለ. በይሁዳ ዘመን ስለ ነበሩ ክሓዲዎች የተሰጠ መግለጫ (8-16)
      (1) ስም የማጥፋት ንግግራቸው ተወገዘ (8-10)
      (2) ባሕርያቸው በሥዕላዊ መልክ ተገለጠ (11-13)
      (3) እንደሚጠፉ ተተነበየ (14-16)
4. ለእማኞች የተሰጠ ምክር (17-23)
5. የመጨረሻ ቡራኬ (24-25)

1 የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋይና የያዕቆብ ወንድም ይሁዳ፤

ለተጠሩት፣ በእግዚአብሔር አብ ለተወደ ዱትና በኢየሱስ ክርስቶስ ለተጠበቁት[ሀ]፤

2ምሕረት፣ ሰላምና ፍቅር ይብዛላችሁ።

**የዐመፀኞች ኀጢአትና የሚጠብቃቸው ፍርድ**

3ወዳጆች ሆይ፤ አብረን ስለምንካፈለው ድነት ልጽፍላችሁ እጅግ ጓጒቼ ነበር፤ ነገር ግን ለቅዱሳን አንዴና ለመጨረሻ ስለ ተሰጠው እምነት እንድትጋደሉ ለመምከር እጽፍ ላችሁ ዘንድ ግድ ሆነብኝ። 4ከረጅም ጊዜ በፊት ለዚህ ፍርድ[ለ] የተጻፉ አንዳንድ ሰዎች ሾልከው ወደ እናንተ ገብተዋልና፤ እነርሱ ፈሪሀ እግዚአብሔር የሌላቸው፣ የአምላካችንን ጸጋ በርኵሰት የሚለውጡና እርሱ ብቻ ልዑል ገዣችንና ጌታችን የሆነውን ኢየሱስ ክርስቶስን የሚክዱ ናቸው።

5ምንም እንኳ አስቀድማችሁ ይህን ሁሉ የምታውቁ ቢሆንም፣ ጌታ[ሐ] ሕዝቡን ከግብፅ ምድር እንዴት እንዳወጣ፣ በኋላ ግን ያላመኑትን እንዳጠፋ ላስታውሳችሁ እወ ዳለሁ። 6የሥልጣን ስፍራቸውን ያልጠበቁ ትን ነገር ግን መኖሪያቸውን የተዉትን መላእክት በዘላለም እስራት እስከ ታላቁ ቀን ፍርድ ድረስ በጨለማ ጠብቆአቸዋል። 7እንዲሁም ሰዶምና ገሞራ፣ በዙሪያቸውም ያሉ ከተሞች ለሴሰኛነትና ከተፈጥሮ ሥር ዐት ውጭ ለሆነ ሩካቤ ሥጋ ራሳቸውን አሳልፈው ሰጡ፤ እነርሱም በዘላለም እሳት በመቀጣት ለሚሠቃዩት ምሳሌ ሆነዋል።

8በዚህ ሁኔታ እነዚህ ሕልም አላሚዎች የገዛ ሥጋቸውን ያረክሳሉ፤ ሥልጣንን ይቃወ ማሉ፤ በሰማይ ክብር ያላቸውንም ፍጥረታት ይሳደባሉ። 9የመላእክት አለቃ የሆነው ሚካኤል እንኳ ስለ ሙሴ ሥጋ ከዲያብሎስ ጋር በተከራ ከረ ጊዜ፣ "ጌታ ይገሥጽህ" አለው እንጂ የስድብ ቃል በመናገር ሊከሰው አልደፈረም። 10እነዚህ ሰዎች ግን የማያውቁትን ነገር ሁሉ ይሳደባሉ፤ አእምሮ እንደሌላቸው እንስሳት በደመ ነፍስ በሚያውቁት ነገር ይጠፋሉ።

11ወዮላቸው! በቃየን መንገድ ሄደዋል፤ ለገንዘብ ሲስገበገቡ በበለዓም ስሕተት ውስጥ

1፡1 ማቴ13፡55፤ የሐ14፡22፤17፡12፤ ሐሥ1፡13፤ሮሜ1፡1፡6፡7
1፡2 ሮሜ1፡7፤ ገላ 6፡16፤1ጢሞ1፡2
1፡3 ቍ20፤ ሐሥ 6፡7፤9፡13፤ 1ቆሮ 10፡14፤ 1ጢሞ6፡12፤ቲቶ1፡4
1፡4 ገላ2፡4፤ ቲቶ1፡16፤2ጴጥ2፡1፤ 1ዮሐ2፡22
1፡5 ዘኍ14፡29፤ ዘዳ 1፡32፤2፡15፤ መዝ 106፡26፤ 1ቆሮ10፡1-5፤ዕብ3፡16-17፤2ጴጥ1፡12፡13፤3፡1-2፤ 1ዮሐ2፡20
1፡6 2ጴጥ2፡4፡9
1፡7 ዘዳ29፡23፤ ማቴ10፡15፤25፡41፤ 2ጴጥ3፡7
1፡8 2ጴጥ2፡10
1፡9 ዘዳ34፡6፤ ዳን10፡13፡21፤12፡1፤ ዘካ3፡2፤1ተሰ4፡16፤ ራእ12፡7
1፡10 2ጴጥ2፡12
1፡11 ዘፍ4፡3-8፤ ዘኍ16፡1-3፡31-35፤ ዕብ11፡4፤2ጴጥ2፡15፤ 1ዮሐ3፡12

[ሀ]1 ወይም የተጠበቁት ሊሆን ይችላል
[ለ]4 ወይም ፍርድ የተመደበላቸውን ሰዎች
[ሐ]5 አንዳንድ የጥንት ቅጆች ኢየሱስ ይላሉ

1 *አገልጋይ፤* የሮሜ1፡1 ማብ ይመ። *የያዕቆብ ወንድም፤* በዚህ መጽሐፍ መግቢያ ላይ "ጸሐፊው" የሚለውን ይመ። *ለተጠሩት* የሮሜ8፡28 ማብ ይመ። *በእግዚአብሔር ... ለተወደዱትና፤* የሐ3፡16፤ ሮሜ8፡28-39 ይመ። *በኢየሱስ ክርስቶስ ለተጠበቁት፤* ፍጥረተ ዓለምን ሁሉ በአንድ ላይ የያዘው እርሱ (ቈላ1፡17፤ ዕብ1፡3)፣ የእግዚአብሔር ልጆች በእምነት ተጠብቀው ዘላለማዊ ርስታቸውን እንደሚወርሱ ያውቃል (ዮሐ6፡37-40፤ 17፡11-12፤ 1ኛጴጥ1፡3-5)።

2 *ሰላም፤* በእግዚአብሔር ጸጋ ውስጥ በመመላለስ የሚገኝ እጅግ የበዛ የውስጥ ዕረፍት ነው (የዮሐ14፡27፤ 20፡19፤ ገላ1፡3፤ ኤፌ1፡2 ማብ ይመ)።

3 *ወዳጆች ሆይ፤* ቍ17 እና 20 እንዲሁም 2ኛጴጥ3፡1 ማብ ይመ። *አብረን ስለምንካፈለው ድነት፤* የይሁዳ የመጀመሪያ ዕቅዱ ስለ አስተምህሮተ ድነት አጠቃላይ ሁኔታ፣ ስለ ሰው ኀጢአትና በደል፣ ስለ እግዚአብሔር ፍቅርና ጸጋ፣ ስለ ኀጢአት ይቅርታና ከዳግም ልደት በኋላ ስለሚገኘው የተለወጠ ሕይወት መጻፍ ነበር። *እምነት፤* እዚህ ላይ በማንኛውም ቦታ ያሉ ክርስቲያኖች የወንጌልን ሐሳብ በሚመለከት የተቀበሉትን እውነት ያመለክታል (በመግቢያው ላይ "መልእክቱ የተጻፈበት ጊዜ" የሚለውን እንዲሁም 1ጢሞ4፡6 ይመ)። ይህን እውነት የሚፈታተኑ ሁኔታዎች በመከሠታቸው መከላከልና መጠበቅ ተገቢ ነበር። *አንዴና ለመጨረሻ ስለ ተሰጠው፤* ይህ እውነት ዘላቂነት ያለውና ሊለወጥ የማይችል ነው።

4 *ለዚህ ፍርድ የተጻፉ፤* ብሉይ ኪዳን እግዚአብሔርን ስማ ይፈሩ ሰዎች ያለውን ተቃውሞ ወይም ሄኖክ የተናገረውን ትንቢት የሚያመለክት ሊሆን ይችላል (ቍ14-15)፤ ወይም ይሁዳ በኀጢ አታቸው ምክንያት ከብዙ ጊዜ በፊት ለዚህ ፍርድ የተመደቡ መሆ ናቸውን ለማመልከት ይሆናል (ሐሳቡን በበለጠ ለመረዳት አማራጭ ትርጕሙንና 2ኛጴጥ2፡3 ይመ)። *ፈሪሀ እግዚአብሔር የሌላቸው፤* ቍ15 እና 18 ይመ። *የአምላካችንን ጸጋ በርኵሰት የሚለውጡ፤* እግዚአብሔር በጸጋው ኀጢአታቸውን እንዲሁ ይቅር ስለሚል ወይም ኀጢአት በአንጻሩ የእግዚአብሔርን ጸጋ ታላቅነት ስለሚያጐላ በጸጋ መዳን ያለገደብ ኀጢአት ለማድረግ ነጻነት እንደ ሰጣቸው ይቈጥራሉ (ከሮሜ5፡20፤6፡1 ጋር ያነጻጽሩ)። *እርሱ ብቻ ልዑል ገዣችንና ጌታችን ... የሚክዱ፤* "ልዑል"የሚለው የተሰጠው የግሪክ ቃል ትርጕም ገደብ የሌሽ ኀይል ወይም ፍጹም የበላይ መሆኑን ይገል ጻል። "ልዑል" እና "ጌታ" የሚሉት ሁለቱ ቃላት ስለ አንድ የሚናገሩ መሆናቸውን የግሪኩ በዋለው ያመለክታል፤ ይህ ጥቅስና ተጓዳኝ ምንባቡም (2ኛ ጴጥ2፡1) ያ ሰው ክርስቶስ መሆኑን በግልጽ አስቀምጦዋል።

*5-7፤* በዚህ ክፍል ውስጥ ሦስት የመለኮታዊ ፍርድ ምሳሌዎች ተጠቅሰዋል።

5 *ያላመኑትን እንዳጠፋ፤* እግዚአብሔር የከነዓንን ምድር እንደሚሰጣቸው አላመኑም፤ ስለዚህ እምነት ያልነበራቸው ጐል ማሶች ሁሉ ወደ ተስፋዪቱ ምድር ሳይገቡ በምድረ በዳ ሞቱ።

6 *የሥልጣን ስፍራቸውን፤* 2ጴጥ2፡4 ማብ ይመ። እግዚ አብሔር ለእያንዳንዱ መልአክ የተለያየ ኀላፊነትና ሥልጣን ሰጥቶ አል (ዳን10፡20-21 ይመ፤ በዚህ ሥፍራ የተጠቀሱ የተለያዩ አለቆች፣ ለተለያዩ ሕዝቦች የተመደቡ መላእክት ሊሆኑ ይችላሉ)። ከእነዚ ህም መላእክት ጥቂቶቹ የተሰጣቸውን ተግባር በመተው ዲያብሎ ስና የእርሱ ጭፍሮች ሆኑ (ከማቴ25፡41 ጋር ያነጻጽሩ)። *መኖሪያ ቸውን፤* መላእክት በተወሰነ ስፍራ የተወሰነ ሥልጣን የነበራቸው ይመስላል። የሰማዩን ግዛት ትተው ወደ ምድር መጥተዋል ብለው የሚገምቱ አሉ (2ጴጥ2፡4 ማብ ይመ)። *መላእክት፤* 2ጴጥ2፡4 ማብ ይመ። *እስራት ... ፍርድ ... ጠብቆአቸዋል፤* 2ጴጥ2፡4 ማብ ይመ። *ታላቁ ቀን፤* የመጨረሻውን ፍርድ ቀን ያመለክታል።

7 *እንዲሁም፤* የሰዶምና ገሞራ ኀጢአት መላእክት ከሠሩት ኀጢአት ወይም የመላእክት ኀጢአት በሰዶምና ገሞራ ከሠሩት ኀጢአት ጋር አንድ ዐይነት ነበር ለማለት አይደለም። ይህ ሐረግ እግዚአብሔር በፍርድ ቀን ኀጢአተኞችን በዘላለም ቅጣት እንደሚቀጣ ለሚያመለክተው ሦስተኛ ገለጻ መግቢያ ነው። *ከተፈጥሮ ሥርዐት ውጪ ለሆነ ሩካቤ፤* ግብረ ሰዶምን የሚያመ ለክት ነው (ዘፍ19፡5 እና ማብ እንዲሁም 2ጴጥ2፡10 ማብ ይመ)። *በዘላለም እሳት በመቀጣት ... ምሳሌ ሆነዋል፤* እግዚ አብሔር የሚቃጠል ድኝ በማፍሰስ ሰዶምንና ገሞራን አጥፍቶአ ቸዋል (ዘፍ19፡24)፤ ይህም ሊመጣ ላለው የዘላለም እሳት ምሳሌ ነው።

8 *ሕልም አላሚዎች፤* እግዚአብሔርን የካዱ ሰዎች በዚህ ስም የተጠሩበት ምክንያት፡- (1) መገለጥ አግኝተናል ስለሚሉ ወይም ደግሞ፣ (2) የራሳቸውን ስሜት በመከተል ከእውነትና ተጨባጭ ከሆነው ነገር የራቁ በመሆናቸው ሊሆን ይችላል። *የገዛ ሥጋቸውን ያረክሳሉ፤* በሰዶምና በገሞራ የነበረውን ግብረ ሰዶ ማዊነት የሚያመለክት ሳይሆን አይቀርም (ቍ4፡7፤ 1ቆሮ6፡18 ይመ)።

*9፤* እንደ ብዙ የቤተ ክርስቲያን አባቶች አመለካከት የዚህ ጥቅስ እርግጠኝነት የተመሠረተው "ዕርገተ ሙሴ" ተብሎ በሚጠራ ው የአዋልድ መጽሐፍ ላይ ነው። መጽሐፍ ቅዱሳዊ ካልሆኑ ሌሎች መጻሕፍት የተወሰዱ የአዲስ ኪዳን ጥቅሶችም አሉ፤ ከእነዚህም ሐዋርያው ጳውሎስ በሐዋ17፡28 (ከአራቱስ)፣ በ1ቆሮ15፡33 (ከሚናንደር) እንዲሁም በቲቶ1፡12 (ከኤፒሜኒደስ) የጠቀሳቸው ይገኙበታል። ይህም፣ እነዚህ ጥቅሶች የተወሰዱበት መጽሐፍ የእግዚአብሔር እስትንፋሳዊ ቃል ነው እንድንል አያደርገንም፤ ነገር ግን የመጽሐፍ ቅዱስ ጸሓፊዎች እነዚህን ጥቅሶች የጠቀሱበት ምክንያት ሐሳባቸውን በሚገባ ለመግለጽ ስለሚያስችሏቸው ብቻ ነው።

10 *የማያውቁትን ነገር ሁሉ፤* 2ጴጥ2፡12 ማብ፤ ከ1ቆሮ2፡14 ጋር ያነጻጽሩ። *አእምሮ እንደሌላቸው እንስሳት፤* 2ጴጥ2፡12 ማብ ይመ።

*11፤* ይሁዳ እንባቢዎቹን ለማስጠንቀቅ ሦስት ተመሳሳ ይነት ያላቸውን የብሉይ ኪዳን ሰዎች በምሳሌነት ይጠቅሳል።

ወድቀዋል፤ በቆሬም ዐመፅ ጠፍተዋል።

[12]እነዚህ ሰዎች በፍቅር ግብዣችሁ ላይ ያሉ እንዳች ኀፍረት ከእናንተ ጋር ቀርበው የሚበሉ ነውረኞች ናቸው፤ ደግሞም ራሳቸውን ብቻ የሚመግቡ እረኞች ናቸው፤ እነርሱም በነፋስ የሚነዱ ዝናብ የሌላቸው ደመናዎች ናቸው፤ በመከር ወራት ፍሬ የማይገኝባቸው ከሥራቸው ተነቅለው ሁለት ጊዜ የሞቱ ዛፎች ናቸው። [13]የነውራቸውን አረፋ የሚደፍቁ፣ የተቈጡ የባሕር ማዕበል፣ ድቅ ድቅ ጨለማ ለዘላለም የሚጠብቃቸው ተንከራታች ከዋክብት ናቸው።

[14]ከአዳም ጀምሮ ሰባተኛ የሆነው ሄኖክ ስለ እነዚህ ሰዎች እንዲህ ሲል ተንብዮአል፤ "እነሆ፤ ጌታ ከእልፍ አእላፋት ቅዱሳኑ ጋር ይመጣል፤ [15]ይህም፣ በሰው ሁሉ ላይ ለመፍረድ እንዲሁም ዐመፀኞችን ሁሉ በክፋት መንገድ በሠሩት የዐመፅ ሥራና በክፋት በእርሱ ላይ ስለ ተናገሩት የስድብ ቃል ሁሉ እጥፊነታቸውን ይፋ ለማድረግ ነው" [16]እነዚህ ሰዎች የሚያጒረመርሙና ሌሎችን ሰዎች የሚከሱ ናቸው፤ ርኩስ ምኞታቸውን ይከተላሉ፤ በራሳቸው ይታበያሉ፤ ጥቅም ለማግኘት ሲሉ ሌሎችን ይክባሉ።

### ጽንቶ ስለ መቆም የቀረበ ጥሪ

[17]ነገር ግን ወዳጆች ሆይ፤ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ሐዋርያት አስቀድመው የተናገሩትን አስታውሱ። [18]እነርሱም፣ "በመጨረሻው ዘመን ርኩስ ምኞታቸውን የሚከተሉ ዘባቾች ይመጣሉ" ብለዋችኋል። [19]እነዚህ ሰዎች በመካከላችሁ መለያየትን የሚፈጥሩ፣ በደመ ነፍስ የሚነዱ መንፈስ የሌላቸው ናቸው።

[20]እናንተ ግን ወዳጆች ሆይ፤ እጅግ ቅዱስ በሆነው እምነታችሁ ራሳችሁን ለማነጽ ትጉ፤ በመንፈስ ቅዱስም ጸልዩ። [21]ወደ ዘላለም ሕይወት የሚያደርሳችሁን የጌታችንን የኢየሱስ ክርስቶስን ምሕረት ስትጠባበቁ ሳለ በእግዚአብሔር ፍቅር ራሳችሁን ጠብቁ።

[22]ተጠራጣሪ ለሆኑት ራሩላቸው፤ [23]እንዳንዶችን ከእሳት ነጥቃችሁ አድኗቸው፤ ለሌሎች ደግሞ በርኩስ ሥጋ የተበከለውን

1፥12 ምሳ25፥14፤ ሕዝ34፥2፡8፡10፤ ማቴ15፥13፤ 1ቆሮ11፥20-22፤ ኤፌ4፥14፤ 2ጴጥ2፥13፡17
1፥13 ኢሳ57፥20፤ ፊል3፥19፤2ጴጥ2፥17
1፥14 ዘፍ5፥18፡21-24፤ዘዳ33፥2፤ ዳን7፥10፤ ዘካ14፥5፤ ማቴ16፥27፤ ዕብ12፥22
1፥15 1ጢሞ1፥9፤ 2ጴጥ2፥6-9
1፥16 ቍ18፤1ቆሮ 10፥10፤2ጴጥ2፥10፡18
1፥17 ኤፌ4፥11፤ ዕብ2፥3፤2ጴጥ3፥2
1፥18 ቍ16፤ 1ጢሞ 4፥1፤ 2ጢሞ3፥1፤ 2ጴጥ2፥1፤3፥3
1፥19 1ቆሮ2፥14፡15
1፥20 ቍ3፤ኤፌ6፥18፤ ቈላ2፥7፤1ተሰ5፥11
1፥21 ማቴ25፥46፤ ቲቶ2፥13፤ዕብ9፥28፤ 2ጴጥ3፥12
1፥23 አሞ4፥11፤ዘካ 3፥2-1፤1ቆሮ3፥15፤ራእ3፥4

*ወዮላቸው!* ፍርድ እንደሚመጣ የተሰጠ ማስጠንቀቂያ ነው (ማቴ23፥13፡15-16፡23፡25፡27፡29)። *በቃየን መንገድ!* የራስ ወዳድነትና የስግብግብነት መንገድ (ዘፍ4፥3 ማብ ይመ) እንዲሁም የጥላቻና የነፍስ ገዳይነት መንገድ ነው (1ዮሐ3፥12 ይመ)። *በበለዓም ስሕተት!* ዐይን ባወጣ ስግብግብነት የተፈጸመውን ስሕተት ያመለክታል (2ጴጥ2፥15 ማብ ይመ)። *በቆሬም ዐመፅ!* ቆሬ እግዚአብሔር በመረጣቸው ሰዎች ላይ ተነሣ ሰው ነበር (ዘኍ16 ይመ)። ይሁዳ፣ በዘመኑ የነበሩት የሐሰት መምህራን በቤተ ክርስቲያን አመራር ላይ ያምፁ እንደ ነበረ የሚጠቍም ይመስላል (ከ3ዮሐ 9-10 ጋር ያነጻጽሩ)።

*12-13!* እነዚህ ጥቅሶች ስድስት ግልጽ የሆኑ ዘይቤዎችን ይዘዋል፤ (1) *በፍቅር ግብዣችሁ ላይ ያለ እንዳች ኀፍረት!* 2ጴጥ2፥13 ማብ ይመ፤ (2) *ራሳቸውን ብቻ የሚመግቡ እረኞች!* በኀላፊነት የተሰጧቸውን በጎች በመመገብ ፈንታ ማለት ነው (ሕዝ34፥8-10ይመ)፤ (3) *ዝናብ የሌላቸው ደመናዎች!* ደመናዎች ደረቁን ምድር ለማርጠብ ተስፋ እንደሚሰጡ ሁሉ የሐሰት መምህራንም ነፍስን የሚያረካ እውነት እንደሚመግቡ ወይም የሕይወት በረከትን እንደሚያወርዱ ተስፋ ይሰጣሉ፤ በተግባር ሲታዩ ግን የሚሰጡት ምንም ነገር የላቸውም፤ (4) *በመከር ወራት ፍሬ የማይገኝባቸው ከሥራቸው ተነቅለው ሁለት ጊዜ የሞቱ ዛፎች ናቸው!* ዛፎቹ ብዙ ፍሬ ማፍራት በሚገባቸው ወቅት ደርቀው መገኘታቸውን ያመለክታል፤ (5) *የተቈጡ የባሕር ማዕበል!* በነፋስ የተገፋ ማዕበል ጥቅም በሌለው ሁኔታ ባለማቋረጥ እንደሚናጋ ሁሉ፣ እነዚህ የሐሰት አስተማሪዎች አእምሮን ለማጕደፍ የማያቋርጥ እንቅስቃሴ ያደርጋሉ (ኢሳ57፥20 ይመ)፤ 6) *ተንከራታች ከዋክብት!* ተወርዋሪ ከዋክብት በሰማይ ላይ ታይተው ወደ ዘላለም ጥፋት እንደሚበሩ ሁሉ፣ እነዚህ የሐሰት መምህራንም ለዘላለማዊ የቢእል ጨለማ የተመደቡ ናቸው።

*14 ከአዳም ጀምሮ ሰባተኛ የሆነው ሄኖክ!* በቃየን የትውልድ ሐረግ ውስጥ የሚገኘውን ሄኖክ ሳይሆን (ዘፍ4፥17)፣ በሴት የትውልድ ሐረግ የሚገኘውን ሄኖክ ያመለክታል (ዘፍ5፥18-24፤ 1ዜና1፥1-3)። አዳም እንደ መጀመሪያ ሰው ከተቈጠረ ሄኖክ ሰባተኛው ይሆናል። ጥቅሱ ምናልባት የተወሰደው በዘፍ5 ላይ የሚገኘው ሄኖክ እንደ ጻፈው ከሚገመተው የአዋልድ መጽሐፍ ከሆነው ከመጽሐፈ ሄኖክ ነው፤ የሄኖክ መጽሐፍ በአዲስ ኪዳን ዘመን ትልቅ ክብር ያለው ጽሑፍ ነበር። በመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖና ውስጥ አልተካተተም ማለት እውነት የለበትም ማለት አይደለም፤ ይሁንና ይሁዳ ከዚህ መጽሐፍ ቢጠቀስም መጽሐፉ የእግዚአብሔር ሥልጣናዊ ቃል መሆኑን አያመለክትም (የዚህን መልእክት መግቢያና የቍ9 ማብ ይመ)። *ተንብዮአል!* መለኮታዊ በሆነ መንገድ አዲስ እውነት መግለጥ ሳይሆን፣ በታወቁት ነገሮች ላይ ተመሥርቶ ወደ ፊት የሚሆነውን ነገር መናገር ማለት ነው (ዳን7፥9-14፤ ዘካ14፥1-5 ይመ)። *ጌታ ... ይመጣል!* ይሁዳ ይህን ጥቅስ ክርስቶስ ዳግም እንደሚመጣና በኃጢአተኞችም ላይ እንደሚፈርድ ለማመልከት ተጠቅሞበታል (2ተሰ1፥6-10 ይመ)፤ *ቅዱሳኑ!* የእግዚአብሔርን መላእክት ሊያመለክት ይችላል (ዳን4፥13-17፤ 2ተሰ1፥7 ይመ)፤ ነገር ግን አንዳንዶች ከጌታ ጋር የሚመለሱ የተነጠቁ ቅዱሳን ናቸው ብለው ያስባሉ (1ተሰ3፥13 ይመ)።

15 *ዐመፀኞችን ... በክፋት መንገድ ... የዐመፅ ... በክፋት!* ይህ ከመጠን ያለፈ ድግግሞሽ በቍ4 ላይ በተጠቀሱት የሐሰት መምህራን ላይ የሚደርሰውን አስፈሪ ፍርድ ያመለክታል።

16 *እነዚህ ሰዎች!* በመጀመሪያ በቍ4 ላይ በተገለጹበት ሁኔታ በድጋሚ "እነዚህ ሰዎች" ተብለው ተጠቅሰዋል (ቍ10፡12፡14፡19፤ ከቍ8 ጋር ያነጻጽሩ)፤ እነርሱም የእግዚአብሔርን ጸጋ የሚያጣምሙ ነውረኛ የሐሰት መምህራን ናቸው።

17 *ሐዋርያት አስቀድመው የተናገሩትን አስታውሱ!* ክርስቲያኖች በእነዚህ እግዚአብሔርን በማይፈሩ ሰዎች መምጣት ብዙም ሊደነቁ አይገባም፤ ይህ እንደሚሆን አስቀድሞ በሐዋርያት ተነግሮአልና (ሐሥ20፥29፤ 1ጢሞ4፥1፤ 2ጢሞ3፥1-5)።

18 *በመጨረሻው ዘመን!* 2ጴጥ3፥3 ማብ ይመ። *ዘባቾች!* በ2ጴጥ3፥3 እና በይሁዳ የተጠቀሱት ዘባቾች ራስ ወዳድነት የተጠናወታቸው ናቸው። *ብለዋችኋል!* ለዚህ የተሰጠው የግሪኩ ቃል እንደዚህ ዐይነት እግዚአብሔርን የማይፈሩ ከሓዲዎች እንደሚመጡ ሐዋርያት ባለማቋረጥ ወይም በተደጋጋሚ እንዳስጠነቀቁ ያመለክታል።

19 *መለያየትን የሚፈጥሩ!* እነዚህ የሐሰት መምህራን እንደ መናፍቃን ሁሉ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ መከፋፈልንና ቡድናዊነትን እንደሚፈጥሩ የሚገልጽ ነው፤ ወይም የግኖስቲክ ፍልስፍና አቀንቃኞች ራሳቸውን እንደ መንፈሳዊ ሌሎችን ደግሞ ተስፋ እንደ ሌላቸው ምድራዊ ሰዎች ይመለከቱ እንደ ነበር የሚያመለክት ሊሆን ይችላል። *በደመ ነፍስ የሚነዱ!* ሌሎችን "ምድራዊ" ብለው የሚጠሩ የሐሰት አስተማሪዎችን የሚገልጽ ምፀታዊ አባባል ነው። *መንፈስ የሌላቸው!* ኖስቲካዊ መምህራን ራሳቸውን መንፈሳዊ አድርገው ይቍጠሩ እንጂ ይሁዳ እንደሚለው መንፈስ ቅዱስ እንኳ የሌላቸው ሰዎች ናቸው፤ የእግዚአብሔር መንፈስ የሌለው ሰው አለመዳኑ ግልጽ ነው (ሮሜ8፥9 ይመ)።

20 *እናንተ ግን ወዳጆች ሆይ!* ይሁዳ በስፋት ከሚያወሳቸው ከሐሰት መምህራኑ ጋር ለማነጻጸር ነው። *ቅዱስ በሆነው እምነታችሁ!* የቍ3 ማብ ይመ። *በመንፈስ ቅዱስም!* እንደ መንፈስ ምሪትና በመንፈስ ኀይል ማለት ነው (ሮሜ8፥26-27፤ ገላ4፥6፤ ኤፌ6፥18 ይመ)።

21 *በእግዚአብሔር ፍቅር ራሳችሁን ጠብቁ!* እግዚአብሔር ክርስቲያኖችን በፍቅሩ ይጠብቃቸዋል (ሮሜ8፥35-39 ይመ)፤ ራሳቸውንም በፍቅሩ እንዲጠብቁ ያስችላቸዋል።

22-23 *ተጠራጣሪ ለሆኑት!* በሐሰት መምህራን የተወሰዱትን ሰዎች ለማሳየት ሊሆን ይችላል።

ልብሳቸውን እንኳ እየጠላችሁ በፍርሀት ምሕረት አሳዩአቸው።

**ቃለ ውዳሴ**

[24]እንዳትወድቁ ሊጠብቃችሁና ያለ ነቀፋና በደስታ በክብሩ ፊት ሊያቀርባችሁ ለሚችለው፣ [25]እርሱ ብቻ አዳኛችን ለሆነው አምላክ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል ከዘመናት ሁሉ በፊት፣ አሁንና እስከ ዘላለምም ድረስ ክብር፣ ግርማ፣ ኀይልና ሥልጣን ይሁን፤ አሜን።

1፥24 ሮሜ16፥25፤ 2ቆሮ4፥14፤ ቈላ1፥22
1፥25 ዮሐ5፥44፤ ሮሜ11፥36፤ 1ጢሞ 1፥17፤ ዕብ13፥8

23 *አንዳንዶችን ከእሳት ነጥቃችሁ፤* በጥፋት አፋፍ ላይ የሚገኙትን ታደጓቸው ማለት ነው። *በርኩስ ሥጋ የተበከለውን ልብሳቸውን፤* የኃጢአተኞች በኃጢአት መበላሸት ከደረፈ ልብሳቸው ጋር ተነጻጽሮአል። *በፍርሀት ምሕረት፤* እንዱ ለሌላው ምሕረት በሚያደርግበት ጊዜ በኃጢአት መፈተን ሊኖር ስለሚችል በጥንቃቄ መሆን እንዳለበት ለማመልከት ነው።

*24-25፤* ይሁዳ በመልእክቱ ውስጥ እግዚአብሔርን የማይፈሩ ሰዎችና የጨለማ ሥራቸውን በሚመለከት መደረግ የሚገባውን ጥንቃቄና ሊወሰድ የሚገባውን ርምጃ ካሳየ በኋላ፣ እምነታቸውን በእርሱ ላይ የሚያደርጉትን ሊጠብቅ ሙሉ በሙሉ በሚችለው በእግዚአብሔር ላይ በማትኮር መልእክቱን ይደመድማል።

# የዮሐንስ ራእይ

## መግቢያ

### ጸሐፊው

ጸሐፊው ዮሐንስ ስለ መሆኑ አራት ጊዜ (1፥1፡4፡9፡22፥8) ተገልጾአል። ስማዕቱ ዮሰጦስ ከነበረበት ከ2ኛው ምእተ ዓመት (ዓ.ም.) ጀምሮ የዚህ መጽሐፍ ጸሐፊ የዘብዴዎስ ልጅ (ማቴ 10፥2) ሐዋርያው ዮሐንስ እንደ ሆነ ሲነገር ቈይቷል። ጸሐፊው አይሁዳዊ፣ ቅዱሳት መጻሕፍትን ጠን ቅቆ የሚያውቅ፣ በትንሹ እስያ በነበሩት ሰባቱ አብያተ ክርስቲያን ዘንድ የታወቀ የቤተ ክርስቲያን መሪና በዓለም ላይ እየሠራ ያለውን ሰይጣናዊ አሠራር የክርስቲያኖች እምነት (ክርስትና) በቅርቡ ድል እንደሚያደርግ የሚያምን መንፈሳዊ ሰው መሆኑን መጽሐፉ ራሱ ይመሰክራል።

ይሁን እንጂ በሦስተኛው ምእተ ዓመት ላይ ዲዮኒሲዮስ የተባለ እንድ አፍሪካዊ ጳጳስ የአቡቀለምሲሱን (የራእየ ዮሐንስ) ቋንቋ፣ የአጻጻፍ ዘዴና ዋና ሐሳብ ከሌሎቹ የዮሐንስ መጻሕፍት ጋር ካነጻጸረ በኋላ፣ ጸሐፊው ሐዋርያው ዮሐንስ ሲሆን እንደማይችል ተናግሯል። እንደ ጳጳሱ አባባል ጸሐፊው በሌሎች የጥንት ጽሑፎች ውስጥ ብዙ ጊዜ ስሙ የተጠቀሰውና ሽማግሌው ዮሐንስ ተብሎ የሚጠራው ሰው ነው። ምንም እንኳ ዛሬም የዲዮኒሲዮስን አመለካከት የሚከተሉ ብዙ ሰዎች ቢኖሩም፣ ውጫዊ ማስረጃዎች ግን ከጥንት የቤተ ክርስቲያን አባቶች ጀምሮ ሲወርድ ሲዋረድ የመጣውን አመለካከት በእጅጉ የሚደግፍ ነው።

### ራእዩ የተጻፈበት ጊዜ

ራእየ ዮሐንስ የተጻፈው ክርስቲያኖች በከፍተኛ ስደት ላይ በነበሩበት ጊዜ ነው። አብዛኛውን ጊዜ የሚጠቀሱት ሁለቱ የስደት ዘመኖች በኔሮ ዘመነ መንግሥት መጨረሻና (54-68 ዓ.ም.) በደሚሺያን ዘመነ መንግሥት መጨረሻ (81-96 ዓ.ም.) ላይ የተከሠቱት ናቸው። በርካታ ሊቃውንት መጽሐፉ የተጻፈው በ95 ዓ.ም. ገደማ እንደ ሆነ ይናገራሉ። ጥቂቶች ደግሞ በቬስፔሺያን ዘመነ መንግሥት (69-79 ዓ.ም) እንደ ተጻፈ ይናገራሉ።

### ዐላማው

በዚያን ዘመን የሮም ባለ ሥልጣኖች ሕዝቡ ንጉሥታትን እንዲያመልክ የሚያስገድድ ዐዋጅ አውጥተው ስለ ነበረ፣ ጌታ ክርስቶስ እንጂ ቄሳር አይደለም የሚሉ አማኞች ከፍተኛ ጥላቻ ገጥሟቸው ነበር። በሰምርኔስ ይኖሩ የነበሩ አማኞች ወደ ፊት ስለሚደርስባቸው መከራ አስቀድሞ ሲነ ገራቸው (2፥10)፣ የፊላድልፍያ ቤተ ክርስቲያንም በዓለም ላይ ሊመጣ ስላለው የፈተና ሰዓት ተነግሯት ነበር (3፥10)። አንቲጳስ ሰማዕት ሆነ (2፥13)፤ ሌሎችም እንዲሁ ሰማዕት ሆኑ (6፥9)። ዮሐንስ የወንጌል አገልጋይ በመሆኑ ብቻ (1፥9)፣ የሮም መንግሥት የቅጣት መፈጸሚያ ሰፍራ ወደ ነበረችው ወደ ፍጥሞ ደሴት ተግዞ (ታስሮ) ነበር። በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የነበሩ አንዳንድ ሐሰተኞች ደግሞ ክርስቲያኖች በሚመጣው መከራ ውስጥ ጸንተው እንዳይቆሙ እምነታቸውን የሚፈታተን ነገር (2፥14-15፡20) ይሰብኩ ነበር።

ዮሐንስ ይህን መጽሐፍ የጻፈው፣ ታማኝ ክርስቲያኖች የነገሥታትን አምልኮ በጽናት እንዲቃወሙ ለመምከር ነው። በእግዚአብሔርና በሰይጣን መካከል የሚደረገው የመጨረሻው ጦርነት በቅርቡ እንደሚደረግም ለአንባቢዎች ገልጾአል። ሰይጣን በአማኞች ላይ የሚደርሰው መከራ እየበዛ እንዲሄድ ቢያደርግም፣ አማኞች ግን እስከ ሞት ድረስ ጸንተው መቆም እንዳለባቸው ይመክራቸዋል። አማኞች ምንም ዐይነት ጕዳት እንዳይደርስባቸው ታትመዋል፤ ክርስቶስ ተመልሶ በሚመጣበት ጊዜ በይፉ ይመሰክርላቸዋል፤ ይህም የሚሆነው የክፉ ኀይሎች ስዘላለም ሲደመሰሱና የእግዚአብሔር ሕዝ ቦች ወደ ዘላለም ክብርና ብፅዕና ሲገቡ ነው።

### ሥነ ጽሑፋዊ ቅርጹ

ተደራስያን ስለ ራእየ ዮሐንስ በቂ ግንዛቤ እንዲኖራቸው ከፈለጉ፣ መጽሐፉ ልዩ ሥነ ጽሑፋዊ ቅርጽ እንዳለው በቅድሚያ መገንዘብ አለባቸው። ራእየ ዮሐንስ አቡቀለምሲስ ማለትም እጅግ ትእምርታዊ (ምሳሌችና ምልክቶች የበዙበት) መጽሐፍ ነው። ምንም እንኳ ራእዩ ለኢትዮጵያ ተደራ ስያን እንግዳ ቢሆንም፣ መጽሐፉ ግን ስራእዮቹና ለትእምርቶቹ የራሱን ትርጓሜ ይሰጣል (ለምሳሌ ከዋክብቱ መላእክት ናቸው፤ መቅረዞቹ አብያተ ክርስቲያናት ናቸው 1፥20፤ "ታላቂቷ ጋለ ሞታ" 17፥1 "ባቢሎን" (ሮም?) ናት 17፥5፡18፤ እንዲሁም ስማያዊቷ ኢየሩሳሌም የበጉ ሚስት ናት 21፥9-10)።

### ልዩ ባሕርያቱ

በመጽሐፉ ውስጥ ቍጥር "ሰባት" አምሳ ሁለት ጊዜ ተጠቅሶ መገኘቱ እንደኛው የመጽሐፉ ልዩ ባሕርይ ነው። ከነዚህም መካከል ሰባት ብፁዓን (የ1፥3 ማብ ይመ)፣ ሰባት አብያተ ክርስቲያናት (1፥4፡11)፣ ሰባት መናፍስት (1፥4)፣ ሰባት የወርቅ መቅረዞች (1፥12)፣ ሰባት ከከቦች (1፥16)፣ ሰባት ማኅተሞች (5፥1)፣ ሰባት ቀንዶችና ሰባት ዐይኖች (5፥6)፣ ሰባት መለከቶች (8፥2)፣ ሰባት ነጐድጓዶች

(10፥3)፣ ሰባት ምልክቶች (12፥1፡3፤ 13፥13-14፤ 15፥1፤ 16፥14፤ 19፥20)፣ ሰባት ዘውዶች (12፥3)፣ ሰባት መቅሠፍቶች (15፥6)፣ ሰባት የወርቅ ጽዋዎች (5፥7)፣ ሰባት ተራሮች (17፥9)፣ ሰባት ነገሥታት (17፥10)፣ እንዲሁም ሌሎች ሰባቶች ይገኙበታል። ሰባት ቍጥር የሚወክለው ፍጹምነትን ነው።

**ትርጓሜ**

የራእየ ዮሐንስ ተርጓሚዎች በአራት ይከፈላሉ፤

1. ***ኀላፍያን፦*** አቡቀለምሲሳዊ ትንቢቶች ሁሉ ገና ድሮ ተፈጽመዋል የሚሉ ናቸው። ራእየ ዮሐንስን የሚመለከቱት በመጀመሪያው ምእተ ዓመት በነበረው ተጨባጭ ሁኔታ መሠረት በመሆኑ፣ በመጽሐፉ ውስጥ የተነገሩት ነገሮች አብዛኞቹ ተፈጽመዋል ይላሉ።

2. ***ታሪካውያን፦*** በየዘመኑ የሚሆነውን የሚናገር መጽሐፍ ነው የሚሉ ናቸው፤ መጽሐፉ በፍጥሞ ከተፈጸመው ድርጊት በመጀመር እስከ ዓለም ታሪክ ፍጻሜ ድረስ ያለውን ረጅም ታሪክ በቅደም ተከተል የሚገልጽ ነው ይላሉ።

3. ***መጻእያን፦*** የወደፊቱን የሚናገር መጽሐፍ ነው የሚሉ ናቸው። መጽሐፉ በመጨረሻው ዘመን ሊሆን ስላለው ነገር የሚያስረዳ ነው ይላሉ።

4. ***ሐሳባውያን፦*** አቡቀለምሲሳዊ ትንቢቶች ትእምርታዊ በመሆናቸው መታየትም ያለባቸው በዚሁ መሠረት ነው የሚሉ ናቸው። በመጽሐፉ ውስጥ የተባሉትን ነገሮች የሚረዱት ትእምርት (ምስልና ምልክት) አድርገው ነው። ትእምርቶቹ ደግሞ በየትኛውም ጊዜና ቦታ (ዘመንና ስፍራ) ተፈጻሚነት አላቸው ይላሉ።

እንደ እውነቱ ከሆነ፣ የራእየ ዮሐንስ መሠረታዊ እውነቶች በየትኛውም ትርጓሜ ላይ የተመረኰዙ አይደሉም። ማንም ሰው በዝርዝር ጉዳዮቹ ሳይተበተብ የመጽሐፉን አጠቃላይ መልእክት መረዳት ይችላል።

**አስተዋፅኦ**

1. *መግቢያ* (1፥1-8)
   - ሀ. *መቅድም* (1፥1-3)
   - ለ. ሰላምታና ውዳሴ (1፥4-8)
2. ኢየሱስ በሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት መካከል (1፥9-20)
3. ለሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት የተላኩ ደብዳቤዎች (ም 2-3)
   - ሀ. ለኤፌሶን (2፥1-7)
   - ለ. ለሰምርኔስ (2፥8-11)
   - ሐ. ለጴርጋሞን (2፥12-17)
   - መ. ለትያጥሮን (2፥18-29)
   - ሠ. ለሰርዴስ (3፥1-6)
   - ረ. ለፊላደልፍያ (3፥7-13)
   - ሰ. ለሎዶቅያ (3፥14-22)
4. ዙፋኑ፣ መጽሐፉና በጉ (ም 4-5)
   - ሀ. በሰማይ ዙፋኑ (ም 4)
   - ለ. በማኅተም የተዘጉት ሰባቱ መጻሕፍት (5፥1-5)
   - ሐ. የታረደው በግ (5፥6-14)
5. ሰባቱ <u>ማኅተሞች</u> (6፥1-8፥1)
   - ሀ. የመጀመሪያው ማኅተም፦ ነጭ ፈረስ (6፥1-2)
   - ለ. ሁለተኛው ማኅተም፦ ቀዩ ፈረስ (6፥3-4)
   - ሐ. ሦስተኛው ማኅተም፦ ጥቁሩ ፈረስ (6፥5-6)
   - መ. አራተኛው ማኅተም፦ ሐመሩ ፈረስ (6፥7-8)
   - ሠ. አምስተኛው ማኅተም፦ ከመሠዊያው በታች ያሉ ነፍሳት (6፥9-11)
   - ረ. ስድስተኛ ማኅተም፦ ታላቅ የምድር መናወጥ (6፥12-17)
   - ሰ. የ144000ው መታተም (7፥1-8)
   - ሸ. እጅግ ብዙ ሕዝብ (7፥9-17)
   - ቀ. ሰባተኛው ማኅተም፦ ዝምታ በሰማይ (8፥1)
6. ሰባቱ <u>መለከቶች</u> (8፥2-11፥19)
   - ሀ. *መግቢያ* (8፥2-5)
   - ለ. የመጀመሪያው መለከት፦ ደም የተቀላቀለበት በረዶና እሳት (8፥6-7)
   - ሐ. ሁለተኛው መለከት፦ ወደ ባሕር የተጣለ አንድ ተራራ (8፥8-9)
   - መ. ሦስተኛው መለከት፦ ምሬት የተባለው ኮከብ (8፥10-11)
   - ሠ. አራተኛው መለከት፦ የፀሐይ፣ የጨረቃና የከዋክብት ሲሶ ተመታ (8፥12-13)

1 ቶሎ መሆን የሚገባውን ነገር ለአገልጋዮቹ እንዲያሳይ፣ እግዚአብሔር ለእርሱ የሰጠው የኢየሱስ ክርስቶስ ራእይ ይህ ነው፤ ኢየሱስም መልእክቱን ልኮ ለአገልጋዩ ለዮሐንስ ገለጠለት፤ [2]እርሱም ስለ እግዚአብሔር ቃልና ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ ምስክርነት ያየውን ሁሉ መሰከረ። [3]ዘመኑ ቀርቦአል፤ እንግዲህ ይህን የትንቢት ቃል የሚያነብ ብፁዕ ነው፤ የሚሰሙትና የተጻፈውንም የሚጠብቁ ብፁዓን ናቸው።

## ሰላምታና ውዳሴ

[4]ከዮሐንስ፤

በእስያ አውራጃ ለሚገኙ ለሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት፤

ካለው፣ ከነበረውና ከሚመጣው፣ በዙፋኑም ፊት ካሉት ከሰባቱ መናፍስት፣[ሀ] [5]እንዲሁም ታማኝ ምስክር፣ ከሙታን በኵርና የምድር ነገሥታት ገዥ ከሆነው ከኢየሱስ ክርስቶስም ጸጋና ሰላም ለእናንተ ይሁን።

ለወደደንና ከኀጢአታችንም በደሙ ነጻ ላወጣን፣ [6]ለአምላኩንና አባቱን እንድናገለግልም መንግሥትና ካህናት ላደረገን፣ ለእርሱ ክብርና ኀይል ከዘላለም እስከ ዘላለም ይሁን! አሜን።

[7]እነሆ፤ በደመና ይመጣል፤
የወጉት እንኳ ሳይቀሩ፣
ዐይን ሁሉ ያየዋል፤
የምድርም ሕዝቦች ሁሉ ከእርሱ የተነሣ
ዋይ ዋይ ይላሉ።
አዎ! ይህ ሁሉ ይሆናል፤ አሜን።

[8]"ያለውና የነበረው፣ የሚመጣውም፣ ሁሉን ቻይ ጌታ አምላክ፣ አልፋና ዖሜጋ እኔ ነኝ" ይላል።

## የሰውን ልጅ የሚመስለው

[9]እኔ ወንድማችሁ ዮሐንስ፣ ከእናንተ ጋር አብሬ በኢየሱስ መከራውንና መንግሥቱን፣ ትዕግሥቱንም ተካፋይ የሆንሁ፣ ስለ እግዚአብሔር ቃልና ስለ ኢየሱስ ምስክርነት ፍጥሞ በምትባል ደሴት ነበርሁ። [10]በጌታ ቀን በመንፈስ ነበርሁ፤ የመለከትን ድምፅ የሚመስል ታላቅ ድምፅ ከበስተ ኋላዬ ሰማሁ፤ [11]ድምፁም፣ "የምታየውን በጥቅልል መጽሐፍ ጽፈህ በኤፌሶን፣ በሰምርኔስ፣ በጴርጋሞን፣ በትያጥሮን፣ በሰርዴስ፣ በፊላድልፍያና በሎዶቅያ ወደሚገኙት ወደ ሰባቱ የእስያ አብያተ ክርስቲያናት ላክ" አለኝ።

[12]እኔም የሚናገረኝን ድምፅ ለማየት ዞር አልሁ፤ ዞር ባልሁም ጊዜ ሰባት የወርቅ መቅረ

1፥1 ቍ4፡9፡19፤ ዳን2፥28፡29፤ ዮሐ12፥49፤17፥8፤ ራእ22፥6፡8፡16
1፥2 ቍ9፤1ቆሮ1፥6፤ ዕብ4፥12፤ራእ6፥9፤ 12፥17፤19፥10
1፥3 ሉቃ11፥28፤ ሮሜ13፥11፤ራእ22፥7
1፥4 ቍ8፡11፡20፤ ኢሳ11፥2፤ሮሜ1፥7፤ ራእ3፥1፤4፥5፡8፤ 5፥6፤11፥17
1፥5 መዝ89፥27፤ ኢሳ55፥4፤ዮሐ18፥37፤ ሮሜ3፥25፤8፥37፤ ቈላ1፥18፤ 1ጢሞ6፥15፤ራእ3፥14
1፥6 ሮሜ11፥36፤ 15፥6፤1ጴጥ2፥5፤ ራእ5፥10፤20፥6
1፥7 ዳን7፥13፤ዘካ 12፥10፤ማቴ16፥27፤ 24፥30፤26፥64፤ዮሐ 19፥34፡37፤ሉቃ17፥ 30፤1ቆሮ1፥7፤1ተሰ 2፥19፤ 4፥16፡17
1፥8 ቍ4፡17፤ራእ4፥8፤ 15፥3፤19፥6፤21፥6፤ 22፥13
1፥9 ቍ1፡2፡6፤ ሐሥ14፥22፤ 2ቆሮ1፥7፤ፊል4፥14፤ 2ጢሞ2፥12፤ዕብ4፥12
1፥10 ዘፀ20፥18፤ ሐሥ20፥7፤ራእ4፥1፡2 ፤17፥3፤21፥10
1፥11 ቍ4፡19፡20፤ሐሥ16፥14፤18፥19፤ቈላ2፥1፤ራእ2፥8፡2፡18፡24፤ 3፥1፡7 1፥12 ቍ20፤ዘፀ25፥31-40፤ዘካ4፥2፤ራእ2፥1

[ሀ]4 ወይም ሰባት ዕጥፍ መንፈስ

1፥1 *ቶሎ መሆን የሚገባውን፤* ቍ 3፤ 22፥6-7፡10፡20 ይመ። *ለአገልጋዮቹ፤* ለአማኞች ሁሉ ነው። *መልእክቱ፤* በሕዝቡና በእርሱ መካከል ሆኖ የሚያገለግል ነው። "መልእክ" የሚለው ቃል በራእየ ዮሐንስ ውስጥ 70 ጊዜ ተጠቅሶአል። *ለዮሐንስ፤* በመጽሐፉ መግቢያ ላይ "ጸሓፊው" የሚለውን ይመ። *የኢየሱስ ክርስቶስ፤* እንዲህ ማለት ሊሆን ይችላል፤ (1) ከኢየሱስ ክርስቶስ፤ (2) ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ፤ ወይም (3) ሁለቱንም። *ራእይ፤* አቡቀለምሲስ ("የተገለጠ" ወይም "ይፋ የሆነ") ማለት ነው።

1፥3 *ዘመኑ ቀርቦአል፤* የያዕ 5፥9 ማብ ይመ። *የትንቢት ቃል፤* ሊመጣ ስላለው ነገር መተንበይ ብቻ ሳይሆን፣ ከእግዚአብሔር የሆነውን ማንኛውንም ቃል መስበክን ይጨምራል፤ ይህም ትእዛዝን፣ ትምህርትን፣ ታሪክንና ትንቢትን ሊሆን ይችላል። *ብፁዓን፤* በዚህ መጽሐፍ ውስጥ "ብፁዓን" የሚለው ቃል ሰባት ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን ይህ የመጀመሪያው ነው (14፥13፤ 16፥15፤ 19፥9፤ 20፥6፤ 22፥7፡14 ይመ)። "ብፁዓን" ሲባል "ደስ የተሰኙ" ከሚለው የላቀና የጠለቀ ትርጕም አለው። እግዚአብሔር ለሰዎች የሰጠውን ልዩ መታደል ወይም በረከት የሚገልጽ ቃል ነው (የመዝ1፥1፤ ማቴ5፥3 ማብ ይመ)። በቍ3 ላይ "ብፁዕ" የሚለው ቃል የተጨመረው የሐሳቡን ፍሰትና የቋንቋውን ዝምድና ለመጠበቅ ነው።

1፥4 *በእስያ፤* በአሁኗ ቱርክ በስተ ምዕራብ የምትገኝ የሮም አውራጃ ናት። *ለሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት፤* አንዱ ከአንዱ የሚርቀው 80 ኪሎ ሜትር ያህል ሲሆን፣ በትንሿ እስያ ውስጥ ከብ ሠርተው የሚገኙ ከተሞች ናቸው፤ በስተ ሰሜን ከምትገኘው ከኤፌሶን ተነሥተን በሰዓትዮሽ አቅጣጫ እየሄድን ወደ ሎዶቅያ (ከኤፌሶን በስተ ምሥራቅ) ብንወጣ ክቡን እንገጥማለን። ምናልባት እነዚህ ከተሞች ሰባት መልክዐ ምድራዊ ክልሎችን የሚያገለግሉ የፖስታ ማዕከሎች ሊሆኑ ይችላሉ። ራእየ ዮሐንስ (ሰባቱን ደብዳቤዎች ጨምሮ) ለእያንዳንዱ ቤተ ክርስቲያን እንደ ተላከ ግልጽ ነው (ቍ11 ይመ)። *ካለው፣ ከነበረውና ከሚመጣውና፤* ከዘፀ 3፥14-15 ላይ የተወሰደና ለእግዚአብሔር የተሰጠውን ስም ባጭሩ የሚያብራራ ነው። ከዕብ 13፥8 ጋር ያነጻጽሩ። *ከሰባቱ መናፍስት፤* እግሬጌ ትርጕሙን ይመ፤ ከዘካ 4፥2፡10 ጋር ያነጻጽሩ።

1፥5 *ጸጋና ሰላም፤* የዮና 4፥2፤ ዮሐ 14፥27፤ 20፥19፤ ገላ 1፥3፤ ኤፌ 1፥2 ማብ ይመ። "ጸጋ" የሚለው ቃል በራእየ ዮሐንስ ውስጥ የተጠቀሰው ሁለት ጊዜ ብቻ (ማለትም እዚህ ላይ እንዲሁም በ22፥21) ሲሆን፣ በጳውሎስ መልእክቶች ውስጥ ግን ከመቶ ጊዜ በላይ ተጠቅሶአል።

1፥6 *መንግሥትና ካህናት፤* በብሉይ ኪዳን ለእስራኤል መጠሪያነት ተሰጥቶ የነበረው ይህ ስም (የዘፀ19፥6፤ ዘካ 3 ማብ ይመ)፤ በአዲስ ኪዳን ለቤተ ክርስቲያን ተሰጥቶአል (1ጴጥ 2፥5፡9)።

1፥7 *የወጉት፤* መዝ 22፥16፤ ኢሳ 53፥5፤ ዘካ 12፥10፤ ዮሐ 19፥34፡37 ይመ። አዎን... አሜን። እጥፍ ድርብ ማረጋገጫ ነው።

1፥8 *ሁሉን ቻይ፤* በአዲስ ኪዳን ውስጥ ዐሥራ ሁለት ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን፣ ዘጠኙ የሚገኙት በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ ነው (እዚሁ ላይ፣ 4፥8፤ 11፥7፤ 15፥3፤ 16፥7፡14፤ 19፥6፡15፤ 21፥22)። የተቀሩት ሦስቱ ደግሞ በሮሜ 9፥29፤ 2ቆሮ 6፥18፤ ያዕ 5፥4 ውስጥ ይገኛሉ። *አልፋና ዖሜጋ፤* የመጀመሪያውና የመጨረሻው የግሪክ ፊደሎች ናቸው። እግዚአብሔር የመጀመሪያም የመጨረሻም ነው (21፥6 ይመ)። እርሱ በሰው ልጆች ታሪክ ሁሉ ላይ ጌታ ነው። በ22፥13 ላይ ኢየሱስ ይሄንኑ ማዕረግ ለራሱ አውሎታል።

1፥9 *መከራውንና መንግሥቱን፣ ትዕግሥቱንም፤* በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ቁልፍ ቃላት ናቸው፤ (1) "መከራውን" (2፥9-10፡22፤ 7፥14)፤ (2) "መንግሥቱን" (11፥15፤ 12፥10፤ 16፥10፤ 17፥12፡ 17-18)፤ (3) "ትዕግሥቱን" (2፥2-3፡19፤ 3፥10፤ 13፥10፤14፥12)። *ፍጥሞ፤* ከኤፌሶን በስተ ደቡብ ምዕራብ 80 ኪሎ ሜትር ያህል ርቃ በኤጂያን ባሕር ውስጥ የምትገኝ (ስድስት በዐሥራ ሁለት ኪሎ ሜትር የምትሆን) ድንጋያማ ደሴት ናት። በወቅቱ ሮማውያን ግዞተኞችን የሚያስሩባት ደሴት ባትሆን አትቀርም። አውሳብዮስ የተባለው፣ "የቤተ ክርስቲያን ታሪክ አባት" (265-340 ዓ.ም.) ዮሐንስ ከእስር የተፈታው በኔርቫ ዘመነ መንግሥት (96-98) እንደ ነበረ ጽፎአል።

1፥10 *በጌታ ቀን፤* ጌታ ከሙታን የተነሣው በዚህ ቀን በመሆኑ፣ ለሳምንቱ የመጀመሪያ ቀን የተሰጠ መደበኛ ስያሜ ነው። ክርስቲያኖች የሚሰበሰቡትም ሆነ (ሐሥ20፥7 ይመ) የርዳታ ገንዘብ የሚያሰባስቡት በዚሁ ቀን ነው (1ቆሮ16፥2 ይመ)። *በመንፈስ፤* እንደ ጴጥሮስ ሕልም እያየ ሳይሆን (የሐሥ10፥10 ይመ) ራእይ እያየ በመንፈሳዊ ልዕልና ውስጥ ነበር።

1፥11 *ጥቅልል መጽሐፍ፤* በመጠን በመጠኑ የተዘጋጁ ፓፒረሶች ወይም ብራናዎች አንድ ላይ ከተሰፉ በኋላ በከላቢት ወይም በማዳወሪያ ይጠነጠናሉ (የዘፀ 17፥14 ማብ ይመ)። ጽሑፎችን በመጽሐፍ መልክ መጠረዝ እስከ ሁለተኛው መቶ ክፍለ ዘመን ድረስ አልተጀመረም ነበር። *ሰባቱ ... አብያተ ክርስቲያናት፤* የቍ 4 ማብ ይመ።

1፥12 *ሰባት፤* በመጽሐፉ መግቢያ ላይ፣ "ልዩ ባሕርያት" የሚለውን ይመ። *የወርቅ መቅረዞች፤* ሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት

ዞችን አየሁ፤ [13]በመቅረዞቹም መካከል "የሰው ልጅ የሚመስል" አየሁ፤ እርሱም እስከ እግሩ የሚደርስ መጐናጸፊያ የለበሰ፣ ደረቱንም በወርቅ መታጠቂያ የታጠቀ ነበር። [14]ራሱና ጠጕሩም እንደ ነጭ የበግ ጠጕር፣ እንደ በረዶም ነጭ ነበሩ፤ ዐይኖቹም የእሳት ነበልባል ይመስሉ ነበር። [15]እግሮቹ በእቶን እሳት የጋለ ናስ ይመስሉ ነበር፤ ድምፁም እንደ ብዙ ወራጅ ውሃ ድምፅ ነበረ። [16]በቀኝ እጁ ሰባት ከዋክብት ይዞ ነበር፤ ከአፉም በሁለት በኩል የተሳለ ሰይፍ ይወጣ ነበር፤ ፊቱም በሙሉ ድምቀቱ እንደሚያበራ ፀሓይ ነበረ።

[17]ባየሁት ጊዜ እንደ ሞተ ሰው ሆኜ በእግሩ ሥር ወደቅሁ። እርሱም ቀኝ እጁን በላዬ ጭኖ እንዲህ አለኝ፤ "አትፍራ፤ የመጀመሪያውም የመጨረሻውም እኔ ነኝ፤ [18]እኔ ሕያው ነኝ፤ ሞቼ ነበር፤ እነሆ አሁን ከዘላለም እስከ ዘላለምድረስ ሕያው ነኝ፤ የሞትና የሲኦል መክፈቻም በእጄ ነው።

[19]"ስለዚህ ያየኸውን፣ አሁን ያለውንና በኋላም የሚሆነውን ጻፍ። [20]በቀኝ እጄ ያየሃቸው የሰባቱ ከዋክብትና የሰባቱ የወርቅ መቅረዞች ምስጢር ይህ ነው፤ ሰባቱ ከዋክብት የሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት መላእክት[a] ናቸው፤ ሰባቱ መቅረዞች ደግሞ ሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት ናቸው።

1፥13 ኢሳ6፥1፤ሕዝ 1፥26፤ዳን7፥13፤ 10፥5፡16፤ራእ2፥1፤ 14፥14፤15፥6
1፥14 ዳን7፥9፤10፥6፤ ራእ2፥18፤19፥12
1፥15 ሕዝ1፥7፤43፥2፤ ዳን10፥6፤ራእ2፥18፤ 14፥2፤19፥6
1፥16 ቁ-20፤ መሳ5፥31፤ኢሳ1፥20፤ 49፥2፤ማቴ17፥2፤ ዕብ4፥12፤ራእ2፥1፡ 12፡16፤3፥1፤19፥15፡21
1፥17 ኢሳ41፥4፤44፥6፤ 48፥12፤ሕዝ1፥28፤ ዳን8፥17፡18፤ ማቴ14፥27፤ራእ2፥8፤ 22፥13
1፥18 ዘዳ32፥40፤ ዳን4፥34፤12፥7፤ ሮሜ6፥9፤ራእ2፥8፤ 4፥9፡10፤9፥1፤10፥6፤ 15፥7፤20፥1
1፥19 ቁ-11፤ዕዝ2፥2
1፥20 ቁ-4፡11፡12፡16፤ ማቴ5፥14፡15
2፥1 ሐሥ18፥19፤ ራእ1፥12፡13፡16
2፥2 ቁ-19፤ 2ቆሮ11፥13፤ 1ዮሐ4፥1፤ ራእ3፥1፡8፡15
2፥3 ዮሐ15፥21
2፥4 ኤር2፥2፤ ማቴ24፥12

## በኤፌሶን ላለው ቤተ ክርስቲያን

**2** "በኤፌሶን ላለው ቤተ ክርስቲያን መልአክ[b] እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

ሰባቱን ከዋክብት በቀኝ እጁ የያዘው፣ በሰባቱም የወርቅ መቅረዞች መካከል የሚመላለሰው እንዲህ ይላል፤ [2]ሥራህን፣ ጥረትህንና ትዕግሥትህን ዐውቃለሁ። ክፉዎችንም ችላ ብለህ እንዳላለፍሃቸው፣ ሐዋርያት ሳይሆኑ ሐዋርያት ነን የሚሉትንም መርምረህ ሐሰተኞች ሆነው እንዳገኘሃቸው ዐውቃለሁ። [3]ደግሞም በትዕግሥት መጽናትህንና ስለ ስሜም መከራን መቀበልህን ዐውቃለሁ፤ በዚህ ሁሉ አልታከትህም።

[4]ይሁን እንጂ የምነቅፍብህ ነገር አለኝ፤ ይኸውም የቀድሞውን ፍቅርህን ትተሃል። [5]እንግዲህ ከየት እንደ ወደቅህ አስብ፤ ንስሓ ገብተህ ቀድሞ ታደርገው የነበረውን ነገር አድርግ፤ ንስሓ ካልገባህ፣ መጥቼ መቅረዝህን ከቦታው እወስድብሃለሁ። [6]ነገር ግን ይህ በጎ ነገር አለህ፤ እኔ የምጠላውን የኒቆላውያንን ሥራ አንተም ጠልተሃል።

2፥5 ቁ-16፡22፤ራእ1፥20፤3፥3፡19 2፥6 ቁ-15

[a]20 ወይም *መልእክተኞች*
[b]1 ወይም *መልእክተኛ*፤ እንዲሁም ቁ-8፣ 12 እና 18

(ቁ- 20 ይመ) ናቸው።

1፥13 *የሰው ልጅ*፤ የዳን 7፥13፤ ማር 8፥31 ማብ ይመ። *እስከ እግሩ ... መጐናጸፊያ*፤ ሊቀ ካህኑ እስከታች እግሩ የሚደርስ መጐናጸፊያ ይለብስ ነበር (ዘፀ 28፥4፤ 29፥5)። ክርስቶስ ሊቀ ካህናት እንደ ሆነ በደረቱ ዙሪያ ያለው የወርቅ መቀነት እንዱ ምስክር ነው።

1፥14 *ነጭ የበግ ጠጕር*፤ ከዳን7፥9፤ ኢሳ1፥18 ጋር ያነጻጽሩ። የሸበተ ጠጕር የጥበብና የክብር ምልክት ነው (ዘሌ19፥32፤ ምሳ 16፥31)። *ዐይኖቹም የእሳት ነበልባል ይመስሉ ነበር*፤ ሁሉን የመመርመር ችሎታ እንዳለው ያሳያል (4፥6 ይመ)።

1፥16 *በሁለት በኩል የተሳለ ሰይፍ*፤ እንደ ረጅሙ የትሬስ ሰዎች በይፍ ነው (2፥12፡16፤ 6፥8፤ 19፥15፡21 ይመ)። በ6፥4፤ 13፥10፡14 ላይ የተጠቀሰው ሰይፍ ግን እንደ ጩቤ ያለ ነው። ሰይፍ መለኮታዊ ፍርድን ያመለክታል (ኢሳ 49፥2፤ ዕብ 4፥12 ይመ)።

1፥17 *በእግሩ ሥር ወደቅሁ*፤ የአክብሮትና የአድናቆት መግለጫ ነው (4፥10፤ 5፥8፤ 7፥11፤ 19፥10፤ 22፥8)። *የመጀመሪያውም የመጨረሻውም*፤ "አልፋና ዖሜጋ" ከሚለው ጋር ተመሳሳይ ነው (ቁ-8፤ ከኢሳ44፥6፤ 48፥12 ጋር ያነጻጽሩ)። *እኔ ነኝ*፤ የዮሐ 6፥35 ማብ ይመ።

1፥18 *ሕያው*፤ በብሉይ ኪዳን "ሕያው አምላክ" በሚለው አገላለጽ ላይ የተመሠረተ ነው (ለምሳሌ ኢያ 3፥10፤ መዝ 42፥2፤ 84፥2 ይመ)። የአረማውያን አማልክት ሙታን ናቸው፤ ክርስቶስ ግን ሕያው ነው። *የሞትና የሲኦል መክፈቻ*፤ በሁለቱም ግዛቶች ላይ ፍጹም ባለ ሥልጣን እንደ ሆነ ያሳያል (ማቴ 16፥18 እና ማብ ይመ)።

*1፥19*፤ በርካታ ሊቃውንት እነዚህን ሦስት ክፍፍሎች የሚመለከቱት የመጽሐፉን አጠቃላይ ውቅር የሚያሳዩ ፍንጮች አድርገው ነው። "ያየኸውን" የሚለው የም1 መክፈቻ ራእይ ነው። "አሁን ያለውንና" የሚለው ደግሞ ለሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት የተጻፈውን ደብዳቤ ነው (ም2-3)። "በኋላም የሚሆነውን" የሚለው ከም4 ጀምሮ ያለውን በሙሉ ነው። ሌሎች ደግሞ ሙሉውን ዐረፍተ ነገር የሚመለከቱት እንደ አንድ አንቀጽ (ከቍ 11 ጋር ያነጻጽሩ) ሲሆን፣ ሁለት ገላጭ ዐረፍተ ነገሮች አሉት ይላሉ። በዚህም መሠረት ጥቅሱ እንዲህ ሊተረጐም ይችላል፣ "ስለዚህ ልታይ ያለውን ነገር ማለትም አሁን ያለውንና ወደፊት የሚሆነውን ነገር ጻፍ"። ይህን ሁለተኛውን አመለካከት የሚደግፉ ሰዎች መጽሐፉን በዚህ መልክ አያዋቅሩትም፤ ምክንያቱም "አሁን" እና "በኋላ" የሚሉት ነገሮች በመጽሐፉ ውስጥ የሚገኙት ተበታትነው ነው።

*1፥20*፤ ለትእምርቶች ትርጓሜ ሊሰጥ ይህ የመጀመሪያው ነው (17፥15፡18 ይመ)። *መላእክት*፤ (1) ሰማያዊ መልእክተኞች፤ ወይም (2) ምድራዊ መልእክተኞች/አገልጋዮች (አግራጌ ትርጕሙን ይመ)፤ ወይም (3) በእያንዳንዱ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ያለውን ድል ነሺ መንፈስ በሰውኛ አገላለጽ ለማመልከት ሊሆን ይችላል።

*2፥1-3፥22*፤ አንዳንዶች ለሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት የተጻፈውን ደብዳቤ የሚረዱት ቤተ ክርስቲያን የምታልፍበትን ጎዳና አስቀድሞ የሚያሳይ ድርጊ አድርገው ነው። ሌሎች ደግሞ ከዮሐንስ ዘመን አንሥቶ እስከ አሁን ድረስ ያሉትን አብያተ ክርስቲያናት ባሕርይን የሚያሳይ አድርገው ነው። ያም ሆነ ይህ እነዚህ አብያተ ክርስቲያናት በአንድ ወቅት በትንሿ እስያ ውስጥ የነበሩ ናቸው። ደብዳቤዎቹ በአጠቃላይ የሚያወሱት ስለ ምስጋና፣ ወቀሳና ዕርማት ነው።

2፥1 *ኤፌሶን*፤ በኤፌሶን መልእክት መግቢያ ላይ፣ "የኤፌሶን ከተማ" የሚለውን ይመ። *መልአክ*፤ የ1፥20 ማብ ይመ። *ሰባቱን ከዋክብት በቀኝ እጁ የያዘው*፤ 1፥16፡20 ይመ። *በሰባቱም የወርቅ መቅረዞች*፤ 1፥12፡20 ይመ።

2፥2 *መርምረህ*፤ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ እውነተኛ አስተምህሮዎችንና ተአማኒ ምክሮችን መርምሮ የመለየት ልማድ ነበር (1ቆሮ14፥29፤1ተሰ 5፥21፤1ዮሐ 4፥1 ይመ)።

2፥4 *የቀድሞውን ፍቅርህን*፤ እርስ በርስ ወይም ለክርስቶስ የነበራቸውን የመጀመሪያ ፍቅር ነው።

2፥5 *መቅረዝህን ከቦታው እወስድብሃለሁ*፤ ትክክለኛ ፍርድ ነው።

2፥6 *የኒቆላውያንን*፤ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሆነው ከአረማዊው ኅብረተ ሰብ ጋር ተቀላቅሉና መስሉ መኖር ምንም ክፋት የለውም የሚሉ መናፍቃን ናቸው። እነርሱም በክርስቶስ ያገኘነው መንፈሳዊ ነጻነት፣ ጣዖት ለማምለክና ለማመንዘር ወይም ያሻንን ለማድረግ መብት በጥቶናል እያሉ ያበተምሩ ነበር። ሊወርድ ሊዋረድ የመጣው ታሪክ እንደሚያመላው፣ እነዚህ መናፍቃን በኢየሩሳሌም ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ከነበሩት ሰባት ዲያቆናት መካከል አንዱ የሆነውና የአይሁድን እምነት ተቀብሉ የነበረው የአንጾኪያው ኒቆላዎስ ተከታዮች ናቸው (ሐሥ6፥5)፤ ይሁንና ይህ በአጋጣሚዎች ላይ የተመሠረተ አስተያየት ነው። በጴርጋሞን የበለዓምን ትምህርት የሚከተሉ ቍ14-15፣ በትያጥሮን ደግሞ የኤልዛቤልን መን

[7]መንፈስ ለአብያተ ክርስቲያናት የሚና ገረውን፣ ጆሮ ያለው ይስማ፤ ድል ለሚነሣ በእግዚአብሔር ገነት ካለው ከሕይወት ዛፍ እንዲበላ አደርገዋለሁ።

## በሰምርኔስ ላለው ቤተ ክርስቲያን

[8]"በሰምርኔስ ላለው ቤተ ክርስቲያን መልአክ እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

የመጀመሪያውና የመጨረሻው፣ ሞቶም የነበረውና ሕያው የሆነው እንዲህ ይላል፤ [9]መከራህንና ድኽነትህን ዐውቃለሁ፤ ይሁን እንጂ ሀብታም ነህ፤ አይሁድ ሳይሆኑ አይሁድ ነን እያሉ ስምህን የሚያጠፉትን ዐውቃለሁ፤ እነርሱ ግን የሰይጣን ማኅበር ናቸው። [10]ሊደርስብህ ያለውን መከራ አትፍራ። እነሆ፤ ዲያብሎስ ሊፈትናችሁ አንዳንዶቻችሁን ወደ እስር ቤት ይጥላል፤ ዐሥር ቀንም መከራ ትቀበላላችሁ። እስከ ሞት ድረስ ታማኝ ሁን፤ እኔም የሕይወትን አክሊል እሰጥሃለሁ።

[11]መንፈስ ለአብያተ ክርስቲያናት የሚናገረውን ጆሮ ያለው ይስማ፤ ድል የሚነሣም በሁለተኛው ሞት ከቶ አይጐዳም።

## በጴርጋሞን ላለው ቤተ ክርስቲያን

[12]"በጴርጋሞን ላለው ቤተ ክርስቲያን መልአክ እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

በሁለት በኩል የተሳለ ስለታም ሰይፍ ያለው እንዲህ ይላል፤ [13]የሰይጣን ዙፋን ባለበት እንደምትኖር ዐውቃለሁ፤ ሆኖም ስሜን አጥብቀህ ይዘሃል። ሰይጣን በሚኖርበት በእናንተ ከተማ የተገደለው ታማኙ ምስክሬ አንቲጳስ በነበረበት ዘመን እንኳ፣ በእኔ ያለህን እምነት አልካድህም።

2፥7 ቍ11:17:29፤ ዘፍ2፥9፤3፥22-24፤ ማቴ11፥15፤ሉቃ23፥43፤ዮሐ16፥33፤ራእ 3፥6:13:22፤13፥9፤ 22፥2:14:19
2፥8 ራእ1፥11:17:18
2፥9 ቍ13:24፤ ማቴ4፥10፤2ቆሮ6፥10፤ ያዕ2፥5፤ራእ3፥9
2፥10 ቍ13፤ዘፍ1፥12፡ 14፤ማቴ10፥22፤ 1ቆሮ9፥25፤ ራእ3፥10፤17፥14
2፥11 ቍ7፤ራእ20፥6፡ 14፤21፥8
2፥12 ቍ16፤1፥11:16
2፥13 ቍ9:24፤ ማቴ4፥10፤ራእ1፥5፤ 11፥3፤14፥12

ገድ የሚከተሉ (ቍ20) ተመሳሳይ መናፍቃን ነበሩ፤ የሁሉንም ትምህርት ብንመለከት ሦስቱም ኒቆላውያን እንደ ነበሩ መገመት ያስችላል። *(printed:* እያጸገትም።)

2፥7 *ድል ለሚነሣ፡* ድል እንዲነሡ የተሰጠው ትእዛዝ በሰባቱም ደብዳቤዎች ላይ ይገኛል (ቍ11:17:26፤3፥5:12:21)። *ገነት፡* ፋርሶች ዐፀደ ደስታን ለመግለጽ ለመጀመሪያ ጊዜ የተጠቀሙበት ቃል ነው (የሉቃ 23፥43 ማብ ይመ) በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ይህ ቃል የሚያመለክተው፣ ኀጢአት ወደ ዓለም ከመግባቱ በፊት በእግዚአብሔርና በሰው መካከል የነበረው ፍጹም ኅብረት በመጨረሻው ዘመን የሚታደስ መሆኑን ነው።

2፥8 *በሰምርኔስ፡* በትንሺ እስያ (በአሁኗ እዝሚር) በራሷ የምትመካ ውብ ከተማ ናት፤ ከሮም ጋር የቅርብ ግንኙነት ስለ ነበራት፣ ነገሥታት እንዲመለኩ ታስገድድ ነበር። ይህ ሁኔታና በከተማዋም ውስጥ ይኖሩ የነበሩ በጥላቻ መንፈስ የተሞሉ በርካታ አይሁዳውያን፣ ክርስቲያን ሆኖ መኖርን ከባድ አድርገውታል። ፖሊካርፕ የተባለው ዕውቅ የጥንት ሰማዕት የሰምርኔስ ቤተ ክርስቲያን ጳጳስ ነበር። *የመጀመሪያውና የመጨረሻው፡* የ1፥17 ማብ ይመ።

2፥9 *አይሁድ ነን እያሉ፡* ሮሜ2፥28-29 ይመ። *የሰይጣን፡* በዕብራይስጥ "ከሳሽ" (ዘካ3፥1 ይመ፤ ከኢዮ1፥6-12፤2፥1-7 ጋር ያነጻጽሩ) ማለት ነው።

2፥10 *መከራ፡* ኢየሱስና (ዮሐ15፥20) ጳውሎስ (2ጢሞ 3፥12) የሰጡትን ማስጠንቀቂያዎች ይመ። *ዲያብሎስ፡* በግሪክ ቋንቋ፣ "ዲያቦሉስ" ማለት ሲሆን ትርጕሙም፣ "ከሳሽ" ማለት ነው። *የሕይወትን አክሊል፡* የዘላለም ሕይወት የሆነውን አክሊል ነው። "አክሊል" የሚለው ቃል የሚያመለክተው ነገሥታት የሚያደርጉትን ዘውድ ሳይሆን (12፥3፤ 13፥1፤ 19፥12)፣ በሩጫ ውድድር አሸናፊ ለሆኑ ሰዎች የሚሰጠውን የአበባ ጕንጕን ነው (3፥11፤ 4፥4:10፤ 6፥2፤ 9፥7፤ 12፥1፤ 14፥14)

2፥11 *ድል የሚነሣም፡* የቍ7 ማብ ይመ። *በሁለተኛው ሞት፡* የእሳት ባሕር ነው (20፥14፤20፥6፤21፥8 ይመ)።

2፥12 *በጴርጋሞን፡* በአሁኑ ጊዜ ቤርጋማ ተብላ ትጠራለች። በጥንት ዘመን የእስያ ዋና ከተማ የነበረች ስትሆን ከአካባቢው ሽለቆአማ ስፍራ 304.6 ሜትር ከፍ ብሎ በሚገኘው ቅንብብ ቅርጽ ባለው ኩረብታማ ተራራ ላይ የታነጸች ከተማ ናት። በግሪክ ቋንቋ ጴርጋሞን ማለት፣ "ግንብ" (መጠበቂያ ስፍራ) ማለት ነው። *በሁለት በኩል የተሳለ ስለታም ሰይፍ፡* የ1፥16 ማብ ይመ።

2፥13 *ታማኙ ምስክሬ፡* በ1፥5 ላይ ለጌታ የተሰጠ ማዕረግ እንደ ሆነ ተጽፎአል። *የሰይጣን ዙፋን ባለበት፡* ጴርጋሞን በእስያ ስግዐት ነገሥታት የሚመለኩባት የአምልኮ ማእከል ስለ ነበረች ሰይጣን ነግሥባታል። *አንቲጳስ፡* በእስያ የመጀመሪያ ሰማዕት ነው። ከቤተ ክርስቲያን ታሪክ እንደምንረዳው፣ አንቲጳስ የተገደለው በዶሚቲያኖስ ዘመነ መንግሥት በናስ መጥበሻ ተጠብሶ ነው።



[14]ይሁን እንጂ የምነቅፍብህ ጥቂት ነገር አለኝ፤ የእስራኤል ልጆች ለጣዖት የተሠዋ ምግብ እንዲበሉና እንዲሴስኑ በፊታቸው መሰናከያ ያስቀምጥ ዘንድ ባላቅን ያስተማረውን የበለዓምን ትምህርት የሚከተሉ አንዳንድ ሰዎች በመካከልህ አሉ፤ [15]የኒቆላውያንን ትምህርት የሚከተሉ ሰዎችም በአንተ ዘንድ አሉ። [16]ስለዚህ ንስሓ ግባ፤ አለዚያ ቶሎ እመጣብሃለሁ፤ በአፌም ሰይፍ እዋጋቸዋለሁ።

[17]መንፈስ ለአብያተ ክርስቲያናት የሚናገረውን ጆሮ ያለው ይስማ፤ ድል ለሚነሣ ከተሰወረው መና እሰጠዋለሁ፤ ደግሞም ከሚቀበለው ሰው በስተቀር ማንም የማያውቀውን አዲስ ስም የተጻፈበት ነጭ ድንጋይ እሰጠዋለሁ።

## በትያጥሮን ላለው ቤተ ክርስቲያን

[18]"በትያጥሮን ላለው ቤተ ክርስቲያን መልእክ እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

እንደ እሳት ነበልባል የሆኑ ዐይኖችና በእሳት ቀልጦ የነጠረ ናስ የሚመስሉ እግሮች ያሉት የእግዚአብሔር ልጅ እንዲህ ይላል፤ [19]ሥራህን፣ ፍቅርህን፣ እምነትህን፣ አገልግሎትህንና ትዕግሥትህን ዐውቃለሁ፤ ደግሞም ከመጀመሪያው ሥራህ ይልቅ የአሁኑ እንደሚበልጥ ዐውቃለሁ።

[20]ይሁን እንጂ የምነቅፍብህ ነገር አለኝ፤ ነቢይ ነኝ የምትለዋን ሴት ኤልዛቤልን ችላ ብለሃታል፤ እርሷ አገልጋዮቼ እንዲሴስኑና ለጣዖት የተሠዋ ምግብ እንዲበሉ በትምህርቷ ታስታቸዋለች። [21]ከዝሙቷ ንስሓ እንድትገባ ጊዜ ሰጥቻት ነበር፤ እርሷ ግን ፈቃደኛ አልሆነችም። [22]ስለዚህ በመከራ ዐልጋ ላይ እጥላታለሁ፤ ከእርሷም ጋር የሚያመነዝሩትን፣ ከመንገዷ ንስሓ ካልገቡ፣ ብርቱ ሥቃይ አመጣባቸዋለሁ፤ [23]ልጆቿንም በሞት እቀጣቸዋለሁ፤ ከዚያም አብያተ ክርስቲያናት ሁሉ እኔ ልብንና ሐሳብን የምመረምር መሆኔን ይረዳሉ፤ ለእያንዳንዳችሁም እንደ ሥራችሁ እከፍላችኋለሁ። [24]ትምህርቷን ሳልተከተላችሁና የሰይጣንም ጥልቅ ምስጢር ነው የሚባለውን ሳልተቀበላችሁ፣ በትያጥሮን ለቀራችሁት ለእናንተ ግን ይህን እላለሁ፤ በእናንተ ላይ ተጨማሪ ሸክም አልጭንባችሁም፤ [25]ብቻ እኔ እስክመጣ ድረስ ያላችሁን አጥብቃችሁ ያዙ።

[26]ድል ለሚነሣና ሥራዬንም እስከ መጨረሻው ለሚፈጽም በሕዝብ ላይ ሥልጣን እሰጠዋለሁ፤ እርሱም፦

[27]'በብረት በትር ይገዛቸዋል፤
እንደ ሸክላ ዕቃም ይፈጫቸዋል፤
ይህም ልክ እኔ ከአባቴ ዘንድ
ሥልጣንን እንደ ተቀበልሁ ነው፤

[28]እኔም የንጋትን ኮከብ እሰጠዋለሁ። [29]መንፈስ ለአብያተ ክርስቲያናት የሚናገረውን ጆሮ ያለው ይስማ።

## በሰርዴስ ላለው ቤተ ክርስቲያን

**3** "በሰርዴስ ላለው ቤተ ክርስቲያን መልእክ[ሀ] እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

ሰባቱን የእግዚአብሔር መናፍስትና[ለ] ሰባቱን ከዋክብት በእጁ የያዘው እንዲህ ይላል፤ ሥራህን ዐውቃለሁ፤ በስም ሕያው ነህ፤ ነገር ግን ሞተሃል። [2]ስለዚህ ንቃ፤

2፥14 ቍ20፤ ሐሥ15፥20፤ 1ቆሮ6፥13፤2ጴጥ2፥15
2፥15 ቍ6
2፥16 ቍ5፤2ተሰ2፥8፤ ራእ1፥16
2፥17 ቍ7፤ኢሳ56፥5፤ 62፥2፤65፥15፤ ዮሐ6፥49፡50፤ 16፥33፤ራእ19፥12
2፥18 ቍ24፤ማቴ4፥3፤ ሐሥ16፥14፤ ራእ1፥11፡14፡15
2፥19 ቍ2
2፥20 ቍ14፤1ነገ16፥31፤ 21፥25፤2ነገ9፥7፤ ሐሥ15፥20
2፥21 ሮሜ2፥4፡5፤ 2ጴጥ3፥9፤ራእ9፥20፤ 16፥9፡11
2፥22 ራእ17፥2፤18፥9
2፥23 1ሳሙ16፥7፤ 1ነገ8፥39፤መዝ139፥1፡ 2፡23፤ምሳ21፥2፤ ኤር17፥10፤ ማቴ16፥27፤ ሉቃ16፥15፤ ሮሜ8፥27፤1ተሰ2፥4
2፥24 ሐሥ15፥28
2፥25 ማቴ16፥27፤ ራእ3፥11
2፥26 መዝ2፥8፤ ማቴ10፥22፤ዮሐ16፥33፤ ራእ3፥21
2፥27 መዝ2፥9፤ ኢሳ30፥14፤ ኤር19፥11፤ራእ12፥5
2፥28 ራእ22፥16
2፥29 ቍ7
3፥1 1ጢሞ5፥6፤ ራእ1፥4፡11፡16፤ ራእ2፥2

[ሀ]1 ወይም መልእክተኛ
[ለ]1 ወይም ሰባት ዕጥፍ መንፈስ

2፥14 *የበለዓምን ትምህርት፤* በለዓም፣ የምድያም ሴቶች እስራኤላውያንን እንዴት እንደሚያስቱ የመከራቸው ሰው ነው (ዘኍ25፥1-2፤31፥16 ይመ፤ ከይሁ11 ጋር ያነጻጽሩ)። እርሱም እግኖች በእምነታቸው ጸንተው እንዳይኖሩ ክፉ ሐሳብን ለሚዘሩ ሐሰተኞች መምህራን ዐይነተኛ ምሳሌ ነው። *ለጣዖት የተሠዋ ምግብ እንዲበሉና እንዲሴስኑ፤* ሐሥ 15፥20፡29 ይመ።

2፥15 *የኒቆላውያንን፤* የቍ 6 ማብ ይመ።

2፥16 *በአፌም ሰይፍ፤* ረጅም ሰይፍ ነው (የ1፥16 ማብ ይመ)።

2፥17 *ከተሰወረው መና፤* ድል ለሚነሡ አማኞች የሚሰጥ ሰማያዊ ምግብ ነው (ከመዝ78፥24 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህም ርኩስ ከሆነው ከበለዓማውያን ምግብ ፍጹም የተለየ ነው። *አዲስ ስም፤* የድል አድራጊው ስም ነው (ኢሳ 62፥2፤ 65፥15 ይመ)። *ነጭ ድንጋይ፤* በጥንት ዘመን የተለያዩ ድንጋዮችን ለምልክትና ለትእምርት መጠቀም የተለመደ ነበር። ነጭ ድንጋይ መሲሑ በሚያዘጋጀው ታላቅ ግብዣ ላይ እንደ፣ "ጥሪ ወረቀት" የሚያገለግል ሳይሆን አይቀርም።

2፥18 *በትያጥሮን፤* የአሁኗ አኪሳር ናት። የጦር ሰፈር እንድትሆን የተቈረቈረችው በቀዳማዊ ሴሌኮስ (311-280 ዓ.ቅ.ክ) ነው፤ ትያጥሮን በልዩ ልዩ የንግድ ምርቶቿ በጣም የታወቀች ከተማ ነበረች። "ቀይ ሐር ሻጭ" የነበረችው ሊድያ (የሐሥ 16፥14 ማብ ይመ) የትያጥሮን ሰው ናት። *እንደ እሳት ነበልባል የሆኑ ዐይኖች፤* የ1፥14 ማብ ይመ፤ ከዳን10፥6 ጋር ያነጻጽሩ። *በእሳት ቀልጦ የነጠረ ናስ፤* የጠራ መዳብ ወይም ናስ ቅይጥ ነው።

2፥20 *ኤልዛቤልን፤* 1ነገ16፥31፤ 2ነገ9፥22፡30-37 ይመ። በጣ ኦብሪ ምዕመናኑ ዘንድ ለታወቀች አንዲት ሴት የተሰጠ ስም ነው፤ እርሷም ለባዕድ አምልኮ ከፍተኛ ስፍራ በመስጠት እግዚአብሔር እንዲናቅ ያደረገች ሴት ናት። *እንዲሴስኑና ለጣዖት የተሠዋ ምግብ እንዲበሉ፤* ቍ 14 ይመ።

2፥22 *በመከራ ዐልጋ፤* አብዛኛውን ጊዜ ታሞ መተኛት የሚታየው የኀጢአት ቅጣት ተደርጎ ነው። (ከ1ቆሮ11፥29-30 ጋር ያነጻጽሩ)።

2፥23 *ልጆቿንም፤* ኤልዛቤል ሕግ የለሽ ወይም ብልሹ ሕይወት ለሚኖሩ ሁሉ መንፈሳዊ እናት ናት። *ልብንና ሐሳብን የምመረምር፤* ከመዝ7፥9፤ ምሳ24፥12፤ ኤር11፥20፤17፥10 ጋር ያነጻጽሩ። እዚህ ላይ፣ "ሐሳብ" (ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ኩላሊት") የሚለው ቃል የሚያመለክተው ፈቃድንና ስሜትን ነው፤ "ልብንና" የሚለው ደግሞ ኅሊናና አእምሮን ነው። *እንደ ሥራችሁ፤* የሚፈረድብን በሠራነው ሥራ መሠረት እንደ ሆነ ኢየሱስ (ማቴ16፥27)፣ ጳውሎስና (ሮሜ2፥6) ዮሐንስ (ራእ18፥6፤ 20፥12-13፤ 22፥12) አስተምረዋል።

2፥24 *የሰይጣንም ጥልቅ ምስጢር ነው የሚባለውን፤* ኖስጥሳውያን (የ1ዮሐ መግቢያ ይመ) እንደሚያስተምሩት አንድ ሰው ሰይጣንን ድል መንሣት ከፈለገ፣ ወደ ሰይጣን ምሽግ ዘልቆ መግባት ማለትም እኩይን በጥልቀት መለማመድ አለበት።

2፥27 *ይገዛቸዋል፤* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ "ይጠብቃቸዋል ወይም እንደ እረኛ ይሆናቸዋል" ማለት ነው (ይህም፣ "ገዛ" ለሚለው ተለዋጭ/ ተምሳሌት ነው)። *በብረት በትር፤* የእገዛዙን ጥንካሬ የሚገልጽ ተምሳሌታዊ አነጋገር ነው (12፥5፤ 19፥15 ይመ።)

3፥1 *በሰርዴስ፤* በአሁኑ ጊዜ ሳርት ተብላ ትጠራለች። የጥንቷ የሊድያ ግዛት እጌ ዋና ከተማ ከመሆኗም በላይ፣ በሀብቷና በዝናዋ በጣም የታወቀች ናት። ሰርዴስ የተቈረቈረችው በጠምሴስ ተራራ ሰሜናዊ ተረተር ላይ ሲሆን፣ ይህም ከአካባቢው ሸለቆማ ስፍራ 457 ሜትር ከፍ ብሎ ይገኛል።

ሊሞት የተቃረበውን የቀረውን ነገር አጽና፤ ሥራህ በአምላኬ ፊት ፍጹም ሆኖ አላገኘሁትም። [3]እንግዲህ የተቀበልኸውንና የሰማኸውን አስታውስ፤ ታዘዘውም፤ ንስሓም ግባ። ባትነቃ ግን እንደ ሌባ እመጣብሃለሁ፤ በየትኛው ሰዓት እንደምመጣብህም አታውቅም።

[4]ነገር ግን ልብሳቸውን ያላሳደፉ ጥቂት ሰዎች በሰርዴስ ከአንተ ጋር አሉ፤ እነርሱም ነጭ ልብስ ለብሰው ከእኔ ጋር ይሄዳሉ፤ ይህ የሚገባቸው ነውና። [5]ድል የሚነሣም እንደ እነርሱ ነጭ ልብስ ይለብሳል፤ እኔም በአባቴና በመላእክቱ ፊት እመሰክርለታለሁ፤ ስሙንም ከሕይወት መጽሐፍ አልደመስስም። [6]መንፈስ ለአብያተ ክርስቲያናት የሚናገረውን ጆሮ ያለው ይስማ።

### በፊላድልፍያ ላለው ቤተ ክርስቲያን

[7]"በፊላድልፍያ ላለው ቤተ ክርስቲያን መልአክ እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

ቅዱስና እውነተኛ የሆነው፣ የዳዊትንም መክፈቻ በእጁ የያዘው እንዲህ ይላል፤ እርሱ የከፈተውን ማንም ሊዘጋው አይችልም፤ የዘጋውንም ማንም ሊከፍተው አይችልም። [8]ሥራህን ዐውቃለሁ፤ እነሆ፤ ማንም ሊዘጋው የማይችል የተከፈተ በር በፊትህ አድርጌአለሁ። ኀይልህ ትንሽ እንደ ሆነ ዐውቃለሁ፤ ሆኖም ቃሌን ጠብቀሃል፤ ስሜንም አልካድህም። [9]እነሆ፣ አይሁድ ሳይሆኑ አይሁድ ነን የሚሉት፣ የሚዋሹት፣ ከሰይጣን ማኅበር የሆኑት ወደ አንተ እንዲመጡ በእግርህ ሥር እንዲሰግዱ፣ እኔ እንደ ወደድሁህም እንዲያውቁ አደርጋለሁ። [10]በትዕግሥት እንድትጸና የሰጠሁህን ትእዛዜን ስለ ጠበቅህ፣ እኔ ደግሞ በምድር ላይ የሚኖሩትን ሊፈትናቸው በዓለም ሁሉ ላይ ከሚመጣው የፈተና ሰዓት እጠብቅሃለሁ።

[11]ቶሎ እመጣለሁ፤ ማንም አክሊልህን እንዳይወስድብህ ያለህን አጥብቀህ ያዝ። [12]ድል የሚነሣውን በአምላኬ ቤተ መቅደስ ውስጥ ዐምድ አደርገዋለሁ፤ ከዚያም ከቶ አይወጣም። የአምላኬን ስምና የአምላኬን ከተማ ስም ይኸውም ከአምላኬ ዘንድ የምትወርደውን የአዲሲቱን ኢየሩሳሌም ስም በእርሱ ላይ እጽፋለሁ፤ አዲሱን ስሜንም በእርሱ ላይ እጽፋለሁ። [13]መንፈስ ለአብያተ ክርስቲያናት የሚናገረውን ጆሮ ያለው ይስማ።

### በሎዶቅያ ላለው ቤተ ክርስቲያን

[14]"በሎዶቅያ ላለው ቤተ ክርስቲያን መልአክ እንዲህ ብለህ ጻፍ፤

አሜን የሆነው፣ ደግሞም ታማኝና እውነተኛ ምስክር የሆነው፣ የእግዚአብሔርም ፍጥረት ገዥ የሆነው እንዲህ ይላል፤ [15]ቀዝቃዛ ወይም ትኩስ እንዳልሆንህ ሥራህን ዐውቃለሁ፤ ቀዝቃዛ ወይም ትኩስ ብትሆን በወደድሁ ነበር። [16]እንግዲህ ለብ ያልህ ብቻ እንጂ ትኩስ ወይም

3፥3 ሉቃ12፥39፤ ራእ2፥5
3፥4 ቆላ5:18፤ይሁ23፤ ራእ4፥4፤6፥11፤7፥9: 13:14፤19፥14
3፥5 ቀላ4፤ማቴ10፥32፤ ዮሐ16፥33፤ራእ20፥12
3፥6 ራእ2፥7
3፥7 ኢሳ22፥22፤ ማቴ16፥19፤ማር1፥24፤ 1ዮሐ5፥20፤ራእ1፥11፤ 6፥10፤19፥11
3፥8 ሐሥ14፥27፤ ራእ2፥2:13
3፥9 ኢሳ43፥4፤49፥23፤ ሮሜ8፥37፤ራእ2፥9
3፥10 ማቴ24፥14፤ 2ጴጥ2፥9፤ራእ2፥10፤ 6፥10፤8፥13፤11፥10፤ 13፥8:14፤17፥8
3፥11 ማቴ16፥27፤ 1ቆሮ9፥25፤ራእ2፥25
3፥12 ሕዝ48፥35፤ ዮሐ16፥33፤ገላ2፥9፤ 4፥26፤ራእ14፥1፤ 21፥2:10፤22፥4
3፥13 ራእ2፥7
3፥14 ምሳ8፥22፤ ዮሐ1፥3፤18፥37፤ ቈላ1፥16:18፤2፥1፤ ራእ1፥5:11
3፥15 ሮሜ12፥11፤ ራእ2፥2

3፥3 *እንደ ሌባ እመጣብሃለሁ፤* የክርስቶስን ዳግም ምጽአት አያመለክትም። ምክንያቱም እዚህ ላይ የክርስቶስ መምጣት የተመሠረተው በቤተ ክርስቲያን ንስሓ መግባትና አለመግባት ላይ ነው። ይሁንና ይህ ሐረግ በአዲስ ኪዳን ውስጥ በሌላ ስፍራ የሚያመለክተው የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ነው (16፥15፤ ማቴ 24፥42-44፤ 1ተሰ5፥2፤ 2ጴጥ3፥10)።

3፥4 *ነጭ ልብስ ለብሰው፤* በክርስቶስ የተቤዡ ሰዎችን ለመ ግለጽ የገባ ነው (3፥18፤ 6፥11፤ 7፥9፤13፤ ይመ፤ እንዲሁም ከ4፥4፤ 19፥14 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥5 *ከሕይወት መጽሐፍ፤* መለኮታዊ መዝገብ ለመጀመሪያ ጊዜ የተጠቀሰው በዘፀ 32፥32-33 ላይ ነው (የመዝ 69፥28 ማብ ይመ፤ ከዳን12፥1ጋር ያነጻጽሩ)። ይህም የመንግሥተ ሰማይ ዜጎች ስም የሚጻፍበት መዝገብ ነው። ስሙ ከዚህ መዝገብ ላይ የተደ መሰሰ ሰው ዜግነቱን ያጣ ሰው ነው (13፥8፤ 17፥8፤ 20፥12:15፤ 21፥27፤ ፊል4፥3 ይመ)።

3፥7 *ፊላድልፍያ፤* በአሁኑ ጊዜ አላሺር ተብላ ትጠራለች። በትንሿ እስያ የምትገኝ ዋነኛ የንግድ ማእከል ከመሆኗም በላይ፣ ለአካባቢው አገሮች እንደመተላለፊያም ታገለግል ነበር። የስሟ ትርጕም፣ "የወንድማማች ፍቅር" ማለት ሲሆን፣ ዳግማዊ አጣለስ (220-130 ዓ.ቅ.ክ) ታማኝነቱን ላሳየው ለወንድሙ ለዳግማዊ አመኔስ መታሰቢያ የሠራት ከተማ ናት። *ቅዱስና እውነተኛ የሆነው፤* 6፥10 ይመ። እግዚአብሔር ቅዱስ አምላክ እንደሆነ በኢሳ 40፥25፤ እና ዕን3፥2-3፤ ማር1፥24 ላይ ይመ። *የዳዊትንም መክፈቻ፤* ክርስቶስ ከዳዊት ወገን የመጣ መሲሕና የመንግሥተ ሰማይ በር ተቈጣጣሪ ነው (ኢሳ 22፥22፤ማቴ16፥19 ይመ)።

3፥8 *የተከፈተ በር፤* እርሱን ለማገልገል የተከፈተ ዕድል ወይም የመንግሥተ ሰማይ በር ነው። ዐውደ ንባቡ ግን ሁለተኛውን ሐሳብ ይደግፋል።

3፥9 *ከሰይጣን ማኅበር፤* የማያምኑትንና ጠላት የሆኑትን አይሁዳውያንን ድፍረት በተሞላበት ተምሳሌታዊ አነጋገር የሚገልጽ ነው። በዮሐ 8፥44 ላይ ኢየሱስ ከተናገረው ብርቱ ተግሣጽ ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም 2ቆሮ 11፥14-15 ይመ። የአይሁድ ምኩራቦች፣ ለማምለኪያ ቃሉን ለማጥኛና ለማኅበራዊ ጕዳዮች ያገለግሉ ነበር። *አይሁድ ነን የሚሉት፤* ሮሜ 2፥28-29 ይመ። *በእግርህ ሥር እንዲሰግዱ፤* በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ አምልኮን የመግለጫ መንገድ ነው (ኢሳ45፥14፤ 60፥14 ይመ፤ ከሐሥ 10፥25፤ ከፊል2፥10 ጋር ያነጻጽሩ፤ የራእ1፥17 ማብ ይመ)።

3፥10 *ከሚመጣው ... እጠብቅሃለሁ፤* ይህን ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ሐረግ፣ "ከዚያ ሰዓት እጠብቅሃለሁ" ወይም፣ "በዚያ ውስጥ እጠብቅሃለሁ" ማለት ሊሆን ይችላል። *የፈተና ሰዓት፤* መንግሥቱ ከመምጣቱ በፊት የሚሆን የፈተና ሰዓት ነው (13፥5-10፤ ማቴ24፥4-28፤ ይመ፤ ከዳን12፥1፤ ማር13፥19፤ 2ተሰ2፥1-12 ጋር ያነጻጽሩ)።

3፥11 *ቶሎ እመጣለሁ፤* ከ1፥1፤ 22፥7:12:20 ጋር ያነጻጽሩ (የያዕ 5፥9 ማብ ይመ)።

3፥12 *ድል የሚነሣውን፤* የ2፥7 ማብ ይመ። *ቤተ መቅደስ፤* የ7፥15 ማብ ይመ። *የአምላኬን ስም፤* 14፥1፤22፥4 ይመ። *አዲሲቱን ኢየሩሳሌም፤* 21፥2:10 ይመ። *አዲሱን ስሜንም በእርሱ ላይ እጽፋለሁ፤* ስም የባሕርይ መግለጫ ነው። አዲሱ የክርስቶስ ስም ክርስቶስ የሰውን ልጆች ለመዋጀት የሆነውን ሁሉ ያመለክታል፤ ይህም ክርስቶስ ተመልሶ በሚመጣበት ጊዜ የሚሰጥ ስም ነው።

3፥14 *ሎዶቅያ፤* በአሁኑ ጊዜ ዴኒዝሊ ተብላ በምትጠራው አጠገብ ትገኛለች። ሮማውያን ዓለምን በሚያስተዳድሩበት ዘመን በፍርግያ የምትገኝ በጣም ሀብታም ከተማ ነበረች። በወቅቱ በባንክ አገልግሎቷ፣ በሕክምና ትምህርቷና በጨርቃ ጨርቅ ምርቷ ትታወቅ ነበር። በውሃ አቅርቦት በኩል ግን ችግር ነበረባት፤ እነዚህ ሁሉ ባሕርያት በመልእክቱ ውስጥ ተንጸባርቀዋል። *አሜን የሆነው፤* ኢሳ 65፥16 "የእውነት አምላክ" ማለትም፣ "እውነት ስለ ሆነው አምላክ" ይናገራል። ይህ አባባል የገባው ፍጹም ታማኝ የሆነውን ለመግለጽ ነው። *ታማኝና እውነተኛ ምስክር የሆነው፤* 1፥5፤ 19፥11 ይመ። *ገዥ የሆነው፤* ይህን ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል ከጊዜ አንጻር ከታየ፣ "መጀመሪያ የሆነው" ሊባል ወይም ከማዕረግ አንጻር ከታየ፣ "ገዥ"ተብሎ ሊተረጐም ይችላል።

3፥16 *ለብ ያልህ ብቻ እንጂ ትኩስ ወይም ቀዝቃዛ ልሆንህ፤* "ትኩስ" የሚለው ቃል በከተማዋ አቅራቢያ የሚ

ቀዝቃዛ ስላልሆንህ ከአፌ አውጥቼ ልተፋህ ነው። [17]‘ሀብታም ነኝ፤ ባለጠጋ ነኝ አንዳችም አያስፈልገኝም’ ትላለህ፤ ነገር ግን ጐስቋላ፣ ምስኪን፣ ድኻ፣ ዕውርና፣ የተራቈትህ መሆንህን አታውቅም። [18]ስለ ዚህ ሀብታም እንድትሆን፣ በእሳት የነ ጠረ ወርቅ እንድትገዛ፣ የዕራቍትነትህ ኀፍረት እንዳይታይ፣ ነጭ ልብስ እንድ ትለብስና ለማየት እንድትችል ዐይንህን በኵል እንድትኳል እመክርሃለሁ።

[19]እኔ የምወዳቸውን እገሥጻለሁ፤ እቀ ጣለሁም። ስለዚህ ትጋ፤ ንስሓም ግባ። [20]እነሆ፤ በደጅ ቆሜ አንኳኳለሁ፤ ማንም ድምፄን ሰምቶ በሩን ቢከፍትልኝ ወደ እርሱ ገብቼ ከእርሱ ጋር እበላለሁ፤ እር ሱም ከእኔ ጋር ይበላል።

[21]እኔ ድል ነሥቼ ከአባቴ ጋር በእ ርሱ ዙፋን ላይ እንደ ተቀመጥሁ፣ ድል የሚነሣውንም ከእኔ ጋር በዙፋኔ ላይ እንዲቀመጥ አደርገዋለሁ። [22]መንፈስ ለአ ብያተ ክርስቲያናት የሚናገረውን ጆሮ ያለው ይስማ።

## በሰማይ ያለው ዙፋን

**4** ከዚህ በኋላ እነሆ በሰማይ የተከፈተ በር አየሁ፤ ቀደም ሲል እንደ መለከት ሲናገረኝ የሰማሁት ድምፅ፣ “ወደዚህ ና፤ ከዚህም በኋላ ሊሆን የሚገባውን ነገር አሳ ይሃለሁ” አለኝ [2]እኔም ወዲያውኑ በመንፈስ ነበርሁ፤ እነሆም፤ በሰማይ ዙፋን ቆሞአል፤ በዙፋኑም ላይ ተቀምጦ ያለ ነበረ። [3]ተቀም ጦ የነበረው የኢያስጲድንና የሰርዲኖን ዕንቍ ይመስል ነበር። የመረግድ ዕንቍ የመሰለ ቀስተ ደመናም ዙፋኑን ከቦት ነበር። [4]በዙፋኑ ዙሪያ ሌሎች ሃያ አራት ዙፋኖች ነበሩ፤ በእነርሱም ላይ ነጭ ልብስ የለበሱና በራሳቸውም ላይ የወርቅ አክሊል የደፉ ሃያ አራት ሽማግሌዎች ተቀምጠው ነበር። [5]ከዙፋኑም መብረቅና ድምፅ፣ ነጐድ ጓድም ወጣ፤ በዙፋኑ ፊት ሰባት መብራ ቶች ይበሩ ነበር፤ እነዚህም ሰባቱ የእግዚአ ብሔር መናፍስት[ሀ] ናቸው። [6]ደግሞም በዙ ፋኑ ፊት እንደ መስተዋት የጠራ የብር ጭቆ ባሕር ነበረ።

በዙፋኑ መካከል፣ በዙሪያውም ከፊትና ከኋላ በዐይን የተሞሉ አራት ሕያዋን ፍጡ ራን ነበሩ። [7]የመጀመሪያው ሕያው ፍጡር አንበሳ፣ ሁለተኛው በሬ ይመስሉ ነበር፤ ሦስተኛው የሰው ፊት የሚመስል ፊት ነበ ረው፤ አራተኛው ደግሞ የሚበር ንስር ይመስል ነበር። [8]አራቱም ሕያዋን ፍጡራን እያንዳንዳቸው ስድስት ስድስት ክንፎች ነበ ሯቸው፤ በዙሪያቸውና በውስጣቸው በዐይ ኖች የተሞሉ ነበሩ፤ ቀንና ሌሊትም፦

3፥17 ምሳ13፥7፤ ሆሴ12፥8፤1ቆሮ4፥8
3፥18 ቈ4፤1ጴጥ1፥7፤ ራእ16፥15
3፥19 ዘዳ8፥5፤ ምሳ3፥12፤ 1ቆሮ11፥32፤ ዕብ12፥5፡ 6፤ራእ2፥5
3፥20 ማቴ24፥33፤ ሉቃ12፥36፤ሮሜ8፥10፤ ያዕ5፥9
3፥21 ማቴ19፥28፤ ዮሐ16፥33፤ራእ5፥5
3፥22 ራእ2፥7
4፥1 ማቴ3፥16፤ ራእ1፥10፡19፤11፥12፡2፡6
4፥2 ቈ9፡10፤ 1ነገ22፥19፤ኢሳ6፥1፤ ሕዝ1፥26-28፤ዳን7፥9፤ ራእ1፥10፤ 20፥11
4፥3 ሕዝ1፥28፤ ራእ10፥1፤21፥11፡19፡20
4፥4 ቈ10፤ራእ3፥4፡ 5፤5፥6፡8፡14፤11፥16፤ 19፥4
4፥5 ዘፀ19፥16፤ ዘካ4፥2፤ራእ1፥4፤ 8፥5፤11፥19፤16፥18
4፥6 ቈ8፡9፤ሕዝ1፥5፡ 18፤10፥12፤ራእ5፥6፤ 6፥1፤7፥11፤14፥3፤ 15፥2፡7፤19፥4
4፥7 ሕዝ1፥10፤ 10፥14

[ሀ]5 ወይም ሰባት ዕጥፍ መንፈስ

ንና ለመድኀኒትነት የሚያገለግለውን ትኵስ ውሃ የሚያመለክት ሊሆን ይችላል። በሎዶቂያ የምትገኘዋ ቤተ ክርስቲያን በመንፈ ሳዊ ሕመም ውስጥ ለሚገኙ ፈውስን፣ በመንፈሳዊ ድካም ውስጥ ለሚገኙ ደግሞ መታደስን ልታስገኝ አልቻለችም። *ልተፋህ!* ቃል በቃል ሲተረጐም፣ “ላስመልስህ ወይም መልሼ ላወጣህ” ማለት ነው።

*3፥18፤* ሎዶቅያ የምትኩራራባቸውን ሦስት ነገሮች ማለ ትም የገንዘብ ሀብቷን፣ የጨርቃ ጨርቅ ምርቷንና ዝናው በዓ ለም ሁሉ የታወቀውን ኵኳን ያወሳል።

3፥19 *እኔ የምወዳቸውን ... እቀጣለሁም፤* ኢዮ5፥17፤ መዝ 94፥12፤ ምሳ3፥11-12፤ 1ቆሮ11፥32፤ ዕብ12፥5-11 ይመ።

3፥20 *በደጅ ቆሜ አንኳኳለሁ፤* አብዛኛውን ጊዜ የሚወሰ ደው፣ ክርስቶስ የማያምኑ ሰዎችን ልብ በር እንደሚያንኳኳ ተደርጎ ነው። በዚህ ዐውደ ንባብ ውስጥ ግን መልእክቱ የተነገ ረው ራሳቸውን ለሚያታልሉ የማኅበረ ምእመናን አባላት ነው።

3፥21 *ድል የሚነሣውንም፤* የ2፥7 ማብ ይመ። *ከእኔ ጋር በዙፋኔ ላይ እንዲቀመጥ!* 20፥4፡6፤ ማቴ19፥28፤ 2ጢሞ2፥12 ይመ።

*4፥1-5፥4!* እነዚህ ሁለት ምዕራፎች ከ6-20 ላሉት ምዕራ ፎች እንደ መግቢያ ያገለግላሉ። በሰማይ ዙፋኑ በሚገኝበት ክፍል፣ ከክፉ ኀይላት ጋር የሚደረገውን የፍጻሜ ጦርነት እንዲ መራ ኀላፊነቱን የተረከበው በጉ ነው፤ በመጨረሻ የሚታየው በጉ ድል ሲነሣና ዲያብሎስም በእሳት ባሕር ውስጥ ሲወረወር ነው።

4፥1 *ወደዚህ ና፤* ልክ እንዲሁ ሙሴም መለኮታዊ መመሪ ያን ከእግዚአብሔር ለመቀበል ወደ ሲና ተራራ ተጠርቶ ወጥቶ አል (ዘፀ 19፥20፡24)። ወደ ሰማይ እንዲወጡ የተጠሩትን ሁለ ቱን ምስክሮች ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (11፥12)። አንዳንድ ሊቃውንት ቤተ ክርስቲያን የምትነጠቀው በዚህ ጊዜ እንደሆነ ይናገራሉ። *ሊሆን የሚገባውን ነገር፤* 1፥1፡19፤ ዳን 2፥28-29፡45 ይመ።

4፥2 *በመንፈስ!* በመንፈሳዊ ልዕልና ውስጥ ነበር (የ1፥10 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 17፥3፤21፥10 ይመ)። *በሰማይ ዙፋን፤* እግ ዚአብሔር ከሰማይ ዙፋኑ ላይ ሆኖ እንደሚገዛ በብሉይ ኪዳን ተደጋግሞ ተገልጾአል (ለምሳሌ መዝ 47፥8 ይመ)።

4፥3 *የኢያስጲድንና የሰርዲኖን ዕንቍ...የመረግድ ዕንቍ!* እግዚአብሔር፣ “ሊቀረብ በማይቻል ብርሃን ውስጥ ይኖራል ... ሊያየውም የሚችል ማንም የለም” (1ጢሞ6፥16) እግዚአብሔ በክብሩ አንጸባራቂ ድንጋዮች ተመስሎ ቀርቦአል፤ ይህም በዙፋኑ ዙሪያ እንደሚያንጸባርቀው ቀስተ ደመና ነው (ከሕዝ 1፥26-28 ጋር ያነጻጽሩ)።

4፥4 *ሃያ አራት ሽማግሌዎች፤* በሰማይ የተሰበሰቡ አማኞ ችን በሙሉ ወይም እግዚአብሔርን የሚያመልኩና የሚያገለግሉ ቅዱሳን መላእክትን የሚወክሉ ናቸው (ቍ9-11፤ 5፥5-14፤ 7፥11-17፤11፥16-18፤ 14፥3፤19፥4 ይመ)። ሃያ አራት የሚለው ቍጥር አብዛኛውን ጊዜ የሚወክለው በብሉይ ኪዳን የነበሩ ዐሥራ ሁለ ቱን የእስራኤል ነገዶችና በአዲስ ኪዳን የነበሩ ዐሥራ ሁለቱን ሐዋ ርያት ነው።

4፥5 *መብረቅና ... ነጐድጓድም!* የእግዚአብሔርን ታላቅ ነትና ኀያልነት የሚገልጽ ተምሳሌት ነው (በሲና ተራራ ላይ የእ ግዚአብሔርን መገለጥ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ፤ ዘፀ19፥16-19 እንዲ ሁም እግዚአብሔር ሕዝቡን ለመቤዠት ሲመጣ ሁኔታውን ለመ ግለጽ የብሉይ ኪዳን ጸሓፊዎች የሚጠቀሙበትን አገላለጽ ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ፤ መዝ18፥12-15፤77፥18)። በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ነጐድጓድና መብረቅ ሁልጊዜ የሚያመለክቱት ከሰማያዊው ቤተ መቅደስ ጋር የተያያዙ ወሳኝ ሁነቶችን ነው። *ሰባቱ ... መናፍስት፤* የ1፥4 ማብ ይመ። “ሰባት” ቍጥር የሙሉነትና የፍጹምነት ምልክት ነው።

4፥6 *የብርጭቆ ባሕር፤* 15፥2 ይመ። ይህ ምስል የተወሰ ደው ከሕዝ 1፥22 ሳይሆን አይቀርም (ከዘፀ24፥10 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ይሁንና ምስሉ በሰማያዊው ቤተ መቅደስ የሚገኘውን ባሕር ሊያ መለክት ይችላል (ከ11፥19፤ 14፥15፡17፤ 15፥5-6፡8፤ 16፥1፡17 ጋር ያነጻጽሩ)፤ ከዚህ ጋር የሚነጻጸረውና በምድራዊው ቤተ መቅ ደስ ውስጥ የሚገኘውም ባሕር ተብሎ ተጠርቶአል (1ነገ7፥23-25፤ 2ነገ16፥17፤ 2ዜና4፥2፡4፡15፡39፤ ኤር27፥19)። በሰማይ በም ትገኘው ቤተ መቅደስ ውስጥ መብራቶች (ቍ 5)፣ መሰዊያ (6፥9)፣ የወርቅ መሠዊያና (8፥3)፣ የኪዳኑ ታቦት (11፥19) እንደ ሚገኙ ተጠቅሶአል። *አራት ሕያዋን ፍጡራን፤* የከበረ ማዕረግ ያላቸው መላእክት ሲሆኑ፣ ሥራቸው ሰማያዊውን ዙፋን መጠበ ቅና እግዚአብሔር እንዲመለክና እንዲወደስ መምራት ነው። *በዐ ይን የተሞሉ፤* ከእይታቸው የሚያመልጥ ምንም ነገር የለም።

*4፥7!* ሕዝቅኤልም በራእዩ እያንዳንዳቸው አራት ፊት ያላ ቸው አራት ሕያዋን ፍጡራን አይቶ ነበር። እነርሱም ከፊት ለፊት የሰው፣ በቀኝ በኩል የአንበሳ፣ በግራ በኩል የበሬ፣ በኋላ በኩል ደግሞ የንስር መልክ ነበራቸው (ሕዝ1፥6፡10)። በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ፍጡራኑ የአንበሳ፣ የበሬና የሚበር ንስር እንዲ

"ቅዱስ፣ ቅዱስ፣ ቅዱስ፣
የነበረው፣ ያለውና የሚመጣው፣
ሁሉን ቻይ ጌታ አምላክ"

ማለትን አያቋርጡም። [9]ሕያዋን ፍጡራኑ በዙፋኑ ላይ ለተቀመጠውና ከዘላለም እስከ ዘላለም ሕያው ሆኖ ለሚኖረው ክብር፣ ሞገስና ምስጋና በሚሰጡበት ጊዜ፣ [10]ሃያ አራቱ ሽማግሌዎች በዙፋኑ ላይ በተቀመጠው ፊት ተደፍተው፣ ከዘላለም እስከ ዘላለም ሕያው ሆኖ ለሚኖረው ይሰግዱ ነበር፤ አክሊላቸውንም በዙፋኑ ፊት አስቀምጠው እንዲህ ይላሉ፤

[11]"ጌታችንና አምላካችን ሆይ፤
ክብርና ሞገስ፣ ኀይልም ልትቀበል
ይገባሃል፤
አንተ ሁሉን ፈጥረሃልና፤
በፈቃድህም ተፈጥረዋልና፤
ሆነዋልምና።"

**ጥቅልል መጽሐፉና በጉ**

**5** በዙፋኑ ላይ የተቀመጠው በውስጥና በውጭ በኩል የተጻፈበት፣ በሰባት ማኅተም የታሸገ ጥቅልል መጽሐፍ በቀኝ እጁ ይዞ አየሁ። [2]አንድ ብርቱ መልአክ በታላቅ ድምፅ፣ "ማኅተሞቹን ለመፍታትና መጽሐፉን ለመክፈት የተገባው ማን ነው?" ብሎ ሲያውጅ አየሁ። [3]ነገር ግን በሰማይም ሆነ በምድር፣ ከምድርም በታች መጽሐፉን ለመክፈት ወይም ገልጦ ለመመልከት የሚችል ማንም አልነበረም። [4]እኔም መጽሐፉን ለመክፈት ወይም ገልጦ ለመመልከት የተገባው ማንም ባለመኖሩ እጅግ አለቀስሁ። [5]ከዚያም ከሽማግሌዎቹ አንዱ፣ "አታልቅስ፤ እነሆ፤ ከይሁዳ ነገድ የሆነው አንበሳ፣ የዳዊት ሥር ድል ነሥቶአል፤ እርሱ መጽሐፉን ሊከፍትና ሰባቱንም ማኅተሞች ሊፈታ ይችላል" አለኝ።

[6]ከዚያም በዙፋኑና በአራቱ ሕያዋን ፍጡራን፣ በሽማግሌዎቹም መካከል የታረደ የሚመስል በግ ቆሞ አየሁ፤ በጉም ሰባት ቀንዶችና ሰባት ዐይኖች ነበሩት፤ እነርሱም ወደ ምድር ሁሉ የተላኩት ሰባቱ የእግዚአብሔር መናፍስት[a] ናቸው። [7]እርሱም መጥቶ በዙፋኑ ላይ ከተቀመጠው ቀኝ እጅ መጽሐፉን ወሰደ። [8]መጽሐፉን በወሰደ ጊዜ አራቱ ሕያዋን ፍጡራን፣ ሃያ አራቱ ሽማግሌዎችም በበጉ ፊት በግምባራቸው ተደፉ፤ እያንዳንዳቸውም የቅዱሳን ጸሎት የሆኑትን በገናና ዕጣን የሞላበትን የወርቅ ሙዳይ ይዘው ነበር። [9]እንዲህም እያሉ አዲስ መዝሙር ዘመሩ፤

"መጽሐፉን ልትወስድ፣
ማኅተሞቹንም ልትፈታ ይገባሃል፤
ምክንያቱም ታርደሃል፤
በደምህም ከነገድ ሁሉ፣ ከቋንቋ ሁሉ፣
ከወገን ሁሉ፣ ከሕዝብ ሁሉ
ሰዎችን ለእግዚአብሔር ዋጅተሃል።
[10]ለአምላካችንም መንግሥትና ካህናት
አደርገሃቸዋል፤
እነርሱም በምድር ላይ ይነግሣሉ።"

[a]6 ወይም ሰባት ዕጥፍ መንፈስ

4፥8 ቍ6፤ኢሳ6፥2፤ 3፤ሕዝ1፥18፤ራእ1፥4፤ 8፥18፤14፥11
4፥9 ቍ2፤41፤መዝ 47፥8፤ራእ1፥18፤5፥1
4፥10 ዘዳ33፥3፤ ራእ1፥18፤5፥1
4፥11 ሐሥ14፥15፤ ራእ1፥6፤5፥12፤10፥6
5፥1 ቍ7፤13፤ ኢሳ29፥11፤ሕዝ2፥9፤ 10፤ዳን12፥4፤ ራእ4፥2፤9፤6፥16
5፥2 ራእ10፥1
5፥5 ዘፍ49፥9፤ ኢሳ11፥1፤10፤ ሮሜ15፥12፤ዕብ7፥14፤ ራእ22፥16
5፥6 ቍ8፤9፤12፤ 13፤ዘካ4፥10፤ዮሐ1፥2 9፤ራእ1፥4፤4፥6
5፥7 ቍ1
5፥8 መዝ141፥2፤ ራእ4፥4፤6፤8፥3፤ 4፤14፥2፤15፥2
5፥9 መዝ40፥3፤98፥1፤ 149፥1፤ኢሳ42፥10፤ 1ቆሮ6፥20፤ዕብ9፥12፤ ራእ4፥11፤13፥7፤ 14፥3፥4
5፥10 1ጴጥ2፥5፤ ራእ3፥21፤20፥4

ሁም የሰው መልክ የሚመስል መልክ አላቸው።

4፥8 *ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ* የኢሳ 6፥3 ማብ ይመ። *የነበረው፣ ያለውና፣ የሚመጣው፤* በዘፀ3፥14-15 ላይ ያለውን መለኮታዊ ስም የሚያብራራ ነው (የራእ 1፥4 ማብ ይመ)። የእግዚአብሔር ኀይልና ቅድስና ከዘላለም እስከ ዘላለም ጸንቶ ይኖራል (ከኢሳ 41፥4 ጋር ያነጻጽሩ)።

4፥10 *አክሊላቸውንም... አስቀምጠው፤* ምስጋናና አምልኮ የሚገባው ለእግዚአብሔር ብቻ እንደ ሆነ የሚገልጽ ነው።

4፥11 *አንተ ሁሉን ፈጥረሃል፤* ዘፍ 1 ይመ።

5፥1 *በውስጥና በውጭ በኩል የተጻፈበት፤* ሕጉ እንደ ተጻፈባቸው የብሉይ ኪዳን ጽላቶች ማለት ነው (ዘፀ32፥15፤ሕዝ 2፥9-10 ይመ)። በጥንት ዘመን ጥቅልል መጻሕፍት የሚሠሩት በመጠን በመጠኑ ከተዘጋጁ ፓፒረሶች ሲሆን፣ በዚህ መልክ የተዘጋጁት ፓፒረሶች የሚሰፉት ደግሞ በጅማት ነው፤ ከፓፒረስ የሚዘጋጁ ጥቅልል መጻሕፍት በውስጥ በኩል የሚሰፉት አግድም በመሆኑ ከውጭ በኩል ይልቅ ለመጻፊያ ምቹ ናቸው። *በሰባት ማኅተም የታሸገ፤* ፈጽሞ ሊጣስ የማይቻል መሆኑን ያመለክታል (ከኢሳ 29፥11፤ ዳን12፥4 ጋር ያነጻጽሩ)። *ጥቅልል መጽሐፍ፤* የ1፥11 ማብ ይመ። በ10፥2፡8-10 ላይ ትንሽ ጥቅልል መጽሐፍ ከሚለው ጋር ያነጻጽሩ።

5፥3 *በሰማይም ሆነ በምድር፣ ከምድርም በታች፤* ዐዋጁ ሁለንታዊ ገጽታ ያለው መሆኑን የሚያመለክት የተለመደ አባባል ነው፤ ይህን ለማድረግ የተገባው አንድም ፍጥረት አልተገኘም፤ ይህ አባባል የግድ በሁለንታ ውስጥ ሦስት ክፍሎች መኖራቸውን ለማስተማር አይደለም (ከዘፀ20፥4፤ፊል2፥10 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥5 *ከይሁዳ ነገድ የሆነው አንበሳ፤* ከዘፍ 49፥8-10 የተወሰደ መሲሐዊ ማዕረግ ነው፤ በዚህ ክፍል ይሁዳ፣ "የአንበሳ ደቦል" እንደ ሆነና፣ "ገዥነት የሚገባው እስኪመጣ ድረስ" የመግዛት መብት ተሰጥቶታል (ሕዝ 21፥27 ይመ)። *የዳዊት ሥር፤* ከዳዊት ወገን የሚወጣውን ታላቅ ንጉሥ በኢሳ11፥1፡10 ይመ። ይህ ማዕረግ በሮሜ 15፥12 ላይ ለመሲሑ የተሰጠ ማዕረግ እንደ ሆነ ተነግሮአል።

5፥6 *የታረደ የሚመስል በግ፤* መታረዱን የሚያሳይ ምልክት አርፎበታል፤ በጉ ሥልጣን የጨበጠው በሞቱ ነው። *በግ፤* የኀጢአት መሥዋዕትና ("እንደ ታረደ"፤ ከኢሳ 53፥7፤ ዮሐ1፥29 ጋር ያነጻጽሩ) ብርቱ አሸናፊ (17፥14) እንደ ሆነ ተገልጾአል። ራእየ ዮሐንስ "በግ" የሚለውን ለመግለጽ የተጠቀመው ልዩ ቃል ነው (ይህ ቃል በራእይ ውስጥ 29 ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን በአዲስ ኪዳን ውስጥ በሌላ ስፍራ የተጠቀሰው 1ጊዜ ብቻ ነው፤ ዮሐ 21፥15)። በጉን እንደ ድል አድራጊና ጦር መሪ መመልከትና ሐሳቡም መንጸባረቅ የጀመረው በአቡቀለምሲሳዊ መጻሕፍት ውስጥ ነው (1ሄኖክ90፥9፤ ኪዳን ዮሴፍ 19፥8)። *ሰባት ቀንዶችና፤* ቀንድ በጥንት አይሁዳውያን ዘንድ የኀይልና የብርታት ምልክት ነው (በዘዳ 33፥17 ጋር ያነጻጽሩ)። ከዳን7፥7:20 ላይ የተጠቀሰው አራተኛው አውሬ ዐሥር ቀንዶች አሉት፤ ከዳን8፥3:5 ጋር ያነጻጽሩ። ሰባት ቀንዶች ሙሉና ፍጹም ብርታትን ያመለክታሉ። *ሰባቱ ... መናፍስት፤* የ4፥5 ማብ ይመ።

5፥8 *የቅዱሳን ጸሎት፤* በአይሁድ እምነት የቅዱሳንን ጸሎት ወደ እግዚአብሔር የሚያቀርቡት መላእክት ናቸው (ጦቢት 12፥15፤ 3ባሮክ11)። *በገናና፤* ዝማሬን ለማጀብ የሚያገለግል የክር ወይም የአውታር መሣሪያ ነው (መዝ33፥2)። *ዕጣን የሞላበትን የወርቅ ሙዳይ፤* ዝርግና ጉድጓዳ መሳይ መሶብ ነው። በዕብራውያን የአምልኮ ሥርዐት ውስጥ ዕጣን የተለመደ ነገር ነው (ዘጸ 33፥10 ይመ፤ ከመዝ141፥2፤ ራእ8፥3-4 ጋር ያነጻጽሩ)።

5፥9 *አዲስ መዝሙር፤* ከ14፥3፤መዝ33፥3፤ 96፥1፤ 144፥9 ኢሳ42፥10 ጋር ያነጻጽሩ። በብሉይ ኪዳን አዲስ መዝሙር የሚዘመረው በረከት ወይም አዲስ መለኮታዊ ተግባር ሲፈጸም ነው። እዚህም ላይ ለመግለጽ የተፈለገው ይሄንኑ ነው፤ የመዝሙሩን ጭብጥ ልብ ይሏል። *በደምህም ... ሰዎችን ... ዋጅተሃል፤* በአዲስ ኪዳን አስተምህሮ ውስጥ የክርስቶስ ሞት ለኀጢአት የቀረበ መሥዋዕት እንደ ሆነ በብዙ ስፍራ ተሰጥቶታል (ማር 10፥45፤ 1ቆሮ6፥20 ይመ)።

5፥10 *መንግሥትና ካህናት፤* የ1፥6 ማብ ይመ። *በምድር ላይ ይነግሣሉ፤* 2፥16-27፤ 20፥4፡6፤ 22፥5 ይመ።

[11]ከዚያም ተመለከትሁ፤ የብዙ መላእክትን ድምፅ ሰማሁ፤ ቍጥራቸውም ሺህ ጊዜ ሺህና እልፍ ጊዜ እልፍ ነበረ፤ እነርሱም በዙፋኑና በሕያዋን ፍጡራኑ፣ በሽማግሌዎቹም ዙሪያ ከበው ነበር፤ [12]በታላቅ ድምፅም እንዲህ ብለው ዘመሩ፤

"የታረደው በግ ኀይልና ባለ ጠግነት፣
ጥበብና ብርታት፣
ክብርና ሞገስ፣ ምስጋናም፣
ሊቀበል ይገባዋል::

[13]ከዚያም በሰማይና በምድር፣ ከምድር በታችና በባሕር፣ በእነርሱ ውስጥ ያሉ ፍጡራንም ሁሉ እንዲህ ብለው ሲዘምሩ ሰማሁ፤

"በዙፋኑ ላይ ለተቀመጠውና ለበጉ፣
ምስጋናና ሞገስ፣ ክብርና ኀይል፣
ከዘላለም እስከ ዘላለም ይሁን::"

[14]አራቱ ሕያዋን ፍጡራንም፣ "አሜን" አሉ፤ ሽማግሌዎቹም በግምባራቸው ተደፍተው ሰገዱ::

## ማኅተሞቹ

6 በጉም ከሰባቱ ማኅተሞች የመጀመሪያውን ሲፈታ አየሁ፤ ከዚያም ከአራቱ ሕያዋን ፍጡራን አንዱ፣ ነጐድጓድ በሚመስል ድምፅ "ና!" ሲል ሰማሁ:: [2]እኔም ተመለከትሁ፤ እነሆ፤ ነጭ ፈረስ ቆሞ ነበር፤ ተቀምጦበት የነበረውም ቀስት ይዞ ነበር፤ አክሊልም ተሰጠው፤ እርሱም እንደ ድል አድራጊ ድል ለመንሣት ወጣ::

[3]በጉ ሁለተኛውን ማኅተም በፈታ ጊዜ፣ ሁለተኛው ሕያው ፍጡር፣ "ና!" ሲል ሰማሁ:: [4]ሌላ ፍም የሚመስል ቀይ ፈረስም ወጣ፤ ተቀምጦበት የነበረው ሰላምን ከምድር ላይ እንዲወስድና ሰዎችም እርስ በርሳቸው እንዲተራረዱ ለማድረግ ሥልጣን ተሰጠው፤ ትልቅም ሰይፍ ተሰጠው::

[5]በጉ ሦስተኛውን ማኅተም በፈታ ጊዜ፣ ሦስተኛው ሕያው ፍጡር፣ "ና!" ሲል ሰማሁ:: እኔም ተመለከትሁ፤ እነሆ፤ ጥቍር ፈረስ ቆሞ አየሁ፤ ተቀምጦበት የነበረውም በእጁ ሚዛን ይዞ ነበር:: [6]ከዚያም ከአራቱ ሕያዋን ፍጡራን መካከል፣ "አንድ እርቦ[ш] ስንዴ ለአንድ ቀን ደመወዝ፤ ሦስት እርቦ ገብስም ለአንድ ቀን ደመወዝ[+] ይሁን፤ ዘይቱንና የወይን ጠጁን አትጕዳ" የሚል ድምፅ ሰማሁ::

[7]በጉ አራተኛውን ማኅተም በፈታ ጊዜ፣ አራተኛው ሕያው ፍጡር፣ "ና!" ሲል ሰማሁ:: [8]እኔም ተመለከትሁ፤ እነሆ፤ ግራጫ ፈረስ ቆሞ አየሁ፤ ተቀምጦበት የነበረው ስሙ ሞት ነበር፤ ሲኦልም ከኋላ ይከተለው ነበር:: እነርሱም በሰይፍ፣ በራብ፣ በመቅሠፍትና በምድር አራዊት እንዲገድሉ በምድር አንድ አራተኛ ላይ ሥልጣን ተሰጣቸው::

[9]አምስተኛውን ማኅተም በፈታ ጊዜ፣ ስለ እግዚአብሔር ቃልና ስለ ጠበቁትም ምስክርነት የታረዱትን ሰዎች ነፍሶች ከመሠዊያው በታች አየሁ:: [10]እነርሱም በታላቅ ድምፅ፣ "ሁሉን የምትገዛ ቅዱስና እውነተኛ ጌታ ሆይ፤ እስከ መቼ አትፈርድም? እስከ መቼስ ደማችንን በምድር በሚኖሩት ላይ አትበቀልም?" አሉ:: [11]ከዚያም ለእያንዳንዳቸው ነጭ ልብስ ተሰጣቸው፤ ወደ ፊት እንደ እነርሱ የሚገደሉ የአገልጋይ ባልንጀሮቻቸውና ወንድሞቻቸው ቍጥር እስኪሞላ ድረስ ጥቂት ጊዜ እንዲታገሡ ተነገራቸው::

[ш]6 ግሪኩ ኮኒክ ይለዋል፤ አንድ ሊትር ገደማ ይሆናል::
[+]6 ግሪኩ አንድ ዲናር ይለዋል::

5፥11 ዳን7፥10፤ ዕብ12፥22፤ ይሁ14፤ ራእ4፥4:6
5፥12 ቍ9፥13፤ ራእ1፥6፤4፥11
5፥13 ቍ1:3:6:7፤ 1ዜና29፥11፤ ሚል1፥6፤ 2፥2፤ ሮሜ11፥36፤ ፊል2፥10፤ ራእ6፥16፤ 7፥10
5፥14 ራእ4፥4:6:9:10
6፥1 ራእ4፥6፤7፤5፥1:16፤ 14፥2፤19፥6
6፥2 መዝ45፥4፤ ዘካ1፥8፤6፥3:11፤ ራእ14፥14፤19፥11: 12
6፥3 ራእ4፥7
6፥4 ዘካ1፥8፤6፥2፤ ማቴ10፥34
6፥5 ዘካ6፥2፤ ራእ4፥7
6፥6 ሕዝ4፥16፤ ራእ4፥6:7፤7፥1:3፤9፥4
6፥7 ራእ4፥7
6፥8 ኤር15፥2:3፤ 24፥10፤ ሕዝ5፥12:17፤ ሆሴ13፥14፤ ዘካ6፥3፤ ራእ1፥18፤20፥13:14
6፥9 ዘፀ29፥12፤ ዘሌ4፥7፤ ሮሜ1፥2፤ ዕብ4፥12፤ ራእ14፥18፤ 16፥7፤20፥4
6፥10 ዘዳ32፥43፤ 2ነገ9፥7፤ መዝ79፥10፤ 119፥84፤ ዘካ1፥12፤ ሉቃ2፥29፤ 2ጴጥ2፥1፤ ራእ3፥7: 10፤16፥6፤ 18፥20፤19፥2
6፥11 ዕብ11፥40፤ ራእ3፥4

5፥11 *ሺህ ጊዜ ሺህና*፤ ከቍጥር በላይ መሆኑን ለመግለጽ የገባ አባባል ነው (ዳን7፥10 ይመ፤ ከዕብ12፥22 ጋር ያነጻጽሩ)::

5፥12 *ኀይልና ... ምስጋናም*፤ ዳዊት በ1ዜና29፥10-19 ላይ ያቀረበውን የስንብት ጸሎት ይመ:: የበጉን ባሕርይ ለመግለጽ የገቡት ቃላት ከሦስት (4፥9-11) ወደ አራት (5፥13) ከዚያም ወደ ሰባት (5፥12፤7፥12) ከፍ ብለዋል::

5፥13 *በሰማይና በምድር፣ ከምድር በታች*፤ የቍ 3 ማብ ይመ::

6፥1 *ከሰባቱ ማኅተሞች*፤ ከሦስቱ ሰባት እጅ ተከታታይ ፍርዶች መካከል የመጀመሪያው ነው፤ በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ሦስት ዐበይት ባለ ሰባት እጅ ፍርዶች ይገኛሉ፤ እነርሱም ሰባቱ ማኅተሞች (6፥1- 8፥5)፣ ሰባቱ መለከቶችና (8፥6-11:19) ሰባቱ ጽዋዎች (16፥1-21) ናቸው::

6፥2 *ነጭ ፈረስ*፤ የአራቱ ፈረሰኞች ምስል የተወሰደው ከዘካ 1፥8-17፤6፥1-8 ላይ ነው (የዘካ6፥2-3 ማብ ይመ):: በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ቀለሞች ከፈረሰኞቹ ባሕርይ ጋር ይዛመዳሉ፤ ለምሳሌ ነጭ የድል አድራጊነት ምልክት ነው:: በነጩ ፈረስ ላይ ስለ ተቀመጠው ፈረሰኛ ከተሰጡት ትርጓሜዎች ውስጥ ዋና ዋናዎቹ (1) ክርስቶስ ነው (ከ19፥11 ጋር ያነጻጽሩ)፤ (2) የክርስቶስ ተቃዋሚ ነው፤ (3) ድል አድራጊው መንፈስ ነው የሚሉት ይገኙበታል:: ሦስተኛው ትርጓሜ ከቀሩት ሦስቱ ፈረሰኞች ጋር ስለሚዛመድ ቅቡልነት ይኖረዋል (የተቀሩት ሦስቱ የሚወክሉት ደም መፋሰስን፣ ራብንና ሞትን ነው):: *ቀስት*፤ የጦር መሣሪያ ነው:: *አክሊልም*፤ የ2፥10 ማብ ይመ::

6፥4 *ሌላ ፍም የሚመስል ቀይ ፈረስ*፤ የደም መፋሰስና የጦርነት ምሳሌ ነው (ከዘካ1፥8፤ 6፥2ጋር ያነጻጽሩ):: *ሰዎችም እርስ በርሳቸው እንዲተራረዱ*፤ ነጩ ፈረስ ከውጭ የሚመጣውን ድል የሚያሳይ ከሆነ፣ ቀዩ ፈረስ ደግሞ ከውስጥ የሚከሰተውን ዐመፅ ያሳያል:: *ሰይፍ*፤ የ1፥16 ማብ ይመ::

6፥5 *ጥቍር ፈረስ*፤ የረሃብ ምሳሌ ነው (ከዘካ6፥2:6 ጋር ያነጻጽሩ):: ስለዚህ ቅደም ተከተሉ ድል፣ ደም መፋሰስና ራብ ይሆናል:: *ሚዛን*፤ በቀኝና በግራ በኩል ከፊት (የሚመዘነውን ነገር ተሸካሚ) ያሉ መመዘኛ መሣሪያ ነው፤ የመጀመሪያዎቹ ሚዛኖች የተሠሩት ከድንጋይ ነበር::

6፥6 *ስንዴ ... ገብስ*፤ አንድ እርቦ ስንዴ የሚበቃው ለአንድ ሰው ብቻ ነው:: ሦስት እርቦ ገብስ ለአንድ ቤተሰብ የሚበቃው ለቅምሻ ያህል ብቻ ነው:: ራብ ሲከሠት ከመደበኛው ዋጋ ቢያንስ ዐሥር እጅ ይጨምራል:: *ዘይቱንና የወይን ጠጁን* በጥቁር ፈረስ ላይ የተቀመጠው ፈረሰኛ የሚያመጣው ጥፋት ገደብ ተጥሎበታል:: የወይራና የወይን ሥሮች በመሬት ውስጥ ጠልቀው ስለሚገቡ በቀላሉ በድርቅ አይጐዱም::

6፥8 *ግራጫ ፈረስ*፤ የሙታንን የገረጣ ገጽታ የሚገልጽ ነው:: የሚያመለክተውም ሞትን ነው:: *ሲኦል*፤ በዕብራይስጥ ሺኦል ማለት ነው (1፥18፤20፥13-14፤ እንዲሁም የማቴ 16፥18 ማብ ይመ)::

6፥9 *ከመሠዊያው በታች*፤ በብሉይ ኪዳን ሥርዐተ አምልኮ መሠረት የታረደው እንስሳ ደም በመሠዊያው ግርጌ እንዲፈስ ይደረግ ነበር (ዘፀ29፥12፤ ዘሌ 4፥7)::

6፥10 *በምድር በሚኖሩት*፤ በራእየ ዮሐንስ ውስጥ የእግዚአብሔርን ጠላቶች ለመግለጽ የገባ አባባል ነው (3፥10፤ 8፥13፤ 11፥10፤ 13፥8:12፤ 17፥2:8 ይመ)::

6፥11 *ነጭ ልብስ*፤ የብፅዕናና የንጽሕና ምሳሌ ነው (3፥5: 18፤4፥4፤ 7፥9:13፤ 19፥14 ይመ):: *ቍጥር እስኪሞላ ድረስ*፤ በአይሁድ እምነት እግዚአብሔር ዓለሙን የሚያስተዳድረው አስቀድሞ በወሰነው የጊዜ ሰሌዳ መሠረት ሲሆን (2ዕዝራ4፥35-37) ፍጻሜ የሚሆነውም የተወሰነ ቍጥር ያላቸው ጻድቃን ሲሞቱ

12ስድስተኛውን ማኅተም ሲፈታ ተመለከትሁ፤ ታላቅ የምድር መናወጥ ሆነ፤ ፀሐይም እንደ ማቅ ጠቈረች:: ጨረቃም በሙሉ እንደ ደም ቀላች፤ 13የበለስ ዛፍ በብርቱ ነፋስ ስትወዛወዝ ያልበሰለው ፍሬ ከእርሷ እንደሚረግፍ፣ የሰማይ ከዋክብት ወደ ምድር ረገፉ:: 14ሰማይ እንደ ጥቅልል መጽሐፍ ተጠቅልሎ ዐለፈ፤ ተራሮችና ደሴቶችም ሁሉ ከስፍራቸው ተወገዱ::

15ከዚህ በኋላ የምድር ነገሥታትና ገዦች፣ የጦር መኰንኖች፣ ሀብታሞች፣ ብርቱዎች፣ ባሮችና ጌቶች ሁሉ በዋሻዎችና በተራሮች ዐለት ውስጥ ተሸሸጉ፤ 16ተራሮቹንና ዐለቶቹንም፣ "በላያችን ውደቁ፤ በዙፋኑ ላይ ከተቀመጠው ፊት ከበጉም ቍጣ ሰውሩን፤ 17ታላቁ የቍጣቸው ቀን መጥቶአልና፤ ማንስ ሊቆም ይችላል?" አሏቸው::

## መቶ አርባ አራት ሺሁ መታተማቸው

7 ከዚህ በኋላ አራት መላእክት በአራቱ የምድር ማእዘኖች ቆመው አየሁ፤ እነርሱም ነፋስ በምድር ወይም በባሕር፣ ወይም በማንኛውም ዛፍ ላይ እንዳይነፍስ አራቱን የምድር ነፋሶች ያዙ:: 2ከዚያም የሕያው እግዚአብሔር ማኅተም ያለው ሌላ መልአክ ከምሥራቅ ሲመጣ አየሁ፤ እርሱም ምድርንና ባሕርን ለመጕዳት ሥልጣን የተሰጣቸውን አራቱን መላእክት በታላቅ ድምፅ እንዲህ አላቸው፤ 3"በአምላካችን አገልጋዮች ግንባር ላይ ማኅተም እስክናደርግባቸው ድረስ ምድርን ወይም ባሕርን፣ ወይም ዛፎችን አትጕዱ::" 4የታተሙትንም ቍጥር ሰማሁ፤ እነርሱም ከእስራኤል ነገዶች ሁሉ መቶ አርባ አራት ሺህ ነበሩ፤

5ከይሁዳ ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከሮቤል ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከጋድ ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
6ከአሴር ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከንፍታሌም ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከምናሴ ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
7ከስምዖን ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከሌዊ ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከይሳኮር ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
8ከዛብሎን ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከዮሴፍ ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ፣
ከብንያም ነገድ ዐሥራ ሁለት ሺህ ታተሙ::

## ነጭ ልብስ የለበሱ እጅግ ብዙ ሕዝብ

9ከዚህም በኋላ አየሁ፤ እነሆ፤ በዙፋኑና በበጉ ፊት ማንም ሊቈጥራቸው የማይችል ከሕዝብ፣ ከነገድ፣ ከወገን፣ ከቋንቋም ሁሉ እጅግ ብዙ ሕዝብ ቆመው ነበር፤ እነርሱም ነጭ ልብስ ለብሰው፣ የዘንባባ ዝንጣፊ በእጃቸው ይዘው ነበር:: 10በታላቅ ድምፅም እንዲህ ብለው ጮኹ፤

"ማዳን በዙፋኑ ላይ የተቀመጠው፣
የአምላካችንና የበጉ ነው::"

11መላእክቱም ሁሉ በዙፋኑና በሽማግሌዎቹ፣ በአራቱም ሕያዋን ፍጡራን ዙሪያ

6፥12 መዝ97፥4፤ ኢሳ29፥6፤50፥3፤ ሕዝ38፥19፤ማቴ24፥29፤ ራእ8፥5፤11፥13፤ 16፥18
6፥13 ኢሳ34፥4፤ ማቴ24፥29፤ ራእ8፥10፤9፥1
6፥14 መዝ46፥2፤ ኢሳ54፥10፤ ኤር4፥24፤ ሕዝ38፥20፤ ናሆ1፥5፤ 2ጴጥ3፥10፤ራእ16፥20፤ 20፥11፤21፥1
6፥15 ኢሳ2፥10:19: 21፤ራእ19፥18
6፥16 ሆሴ10፥8፤ ሉቃ23፥30፤ራእ5፥1
6፥17 መዝ76፥7፤ ኢዩ1፥15፤2፥1:2: 11:31:ናሆ1፥6፤ ሶፎ1፥14:15፤ሚል3፥2፤ ራእ16፥14
7፥1 ኢሳ11፥12፤ ኤር49፥36፤ሕዝ37፥9፤ ዳን7፥2፤ዘካ6፥5፤ ማቴ24፥31፤ራእ6፥6
7፥2 ቍ1፤ማቴ16፥16፤ ራእ9፥4፤14፥1፤22፥4
7፥3 ሕዝ9፥4፤ራእ 6፥6፤9፥4፤14፥1፤ 22፥4
7፥4 ራእ9፥16፤14፥1:3
7፥9 ቍ15፤ራእ3፥4፤ 13፥7
7፥10 መዝ3፥8፤ ራእ5፥1፤12፥10፤ 9፥1
7፥11 ራእ4፥4:6:10

ነው (1ሄኖክ 47፥4)::

6፥12 *የምድር መናወጥ፤* የመለኮትን መምጣት ወይም ጉብኝት የሚገልጽ የተለመደ አባባል ነው (ዘፀ19፥18፤ ኢሳ2፥19፤ ሐጌ2፥6 ይመ):: *ጨረቃም ... እንደ ደም ቀላች፤* ጴጥሮስ በበዓለ ኀምሳ ቀን ባቀረበው ስብከቱ የጠቀሰውን ኢዩ2፥31 ይመ (ሐሥ 2፥20)::

6፥13 *ከዋክብት... ረገፉ፤* የሰው ልጅ ዳግም ከመምጣቱ በፊት ከሚከሰቱት ነገሮች አንዱ ነው (ማር13፥25-26):: *ያልበሰለው ፍሬ፤* በክረምቱ ወራት የበለስ ዛፍ ለምለም ቢሆንም፣ ነፋስ በቀላሉ ስለሚያረግፈው በዚህ ወቅት ምንም ቅጠል አይኖረውም::

6፥14 *ሰማይ እንደ ጥቅልል መጽሐፍ ተጠቅልሎ፤* ኢሳ 34፥4፤ ይመ:: *ተራሮችና ደሴቶች ሁሉ ... ተወገዱ፤* ምናልባት በኤር4፥24 ወይም በናሆ1፥5 እንደ ተባለው ሊሆን ይችላል፤ 16፥20፤ 20፥11 ይመ::

6፥15 *የጦር መኰንኖች፤* አንድ ሺህ ያህል የሚያህሉ ወታደሮችን የሚይዙ የሮማ መኰንኖች ናቸው:: *በዋሻዎች ... ተሸሸጉ፤* ኢሳ 4፥29 ይመ::

6፥16 *ከበጉም ቍጣ፤* በአዲስ ኪዳን አስተምህሮ ውስጥ፣ "የእግዚአብሔር ቍጣ" አንዱ ዐብይ ጭብጥ ነው:: ቍጣው አሁን ተገልጧል (ሮሜ1፥18 ማብ ይመ)፤ ወደ ፊትም ይገለጣል (19፥15 ይመ):: የእግዚአብሔር ቍጣ በብሉይ ኪዳን ነቢያትም ተነግሮአል (ሶፎ1፥14-18፤ ናሆ1፥6፤ ሚል3፥2):: *ከበጉም* የ5፥6 ማብ ይመ::

*7፥1-17፤* የመጨረሻውን ማኅተም ከመጀመሪያዎቹ ስድስት ማኅተሞች የሚለይ ስርዋጽ ወይም መሐል ገብ ሐሳብ ነው፤ ስለ ሰባቱ መለከት በተነገረበት ክፍልም ተመሳሳይ ነገር እናገኛለን፤ 10፥1-10፥13 ይመ:: ይህ ስርዋጽ ሁለት ራእዮችን ይዟል፤ (1) የ144,000 ሰዎችን መታተም (ቍ1-8) እንዲሁም (2) ከቍጥር በላይ የሆነ ሕዝብ (ቍ 9-17)::

7፥1 *አራቱን ... ነፋሶች፤* ከእግዚአብሔር የተላኩ የጥፋት ወኪሎች ናቸው (ኤር 49፥36 ይመ)::

7፥2 *የሕያው አምላክ ማኅተም፤* በጥንት ዘመን ሰነዶች ወይም መዛገቦች በጥንቃቄ ከታጠፉና ከታሰሩ በኋላ መቋጠሪያው በሸክላ ይታሸጋል:: የሰነዱ ላኪ መልእክቱ በማንም እንዳይታይና እንዳይታወቅ በራሱ ስም በተቀረጸ ማኅተም ያትመዋል:: በም 7 የተጠቀሰው ማኅተም በጌታ ተከታዮች ግንባር ላይ የታተመውስ የጌታ ስም እንደ ሆነ ያወሳል (9፥4፤ 14፥1 ይመ፤ ከ22፥4 ጋር ያነጻጽሩ):: የማኅተሙ ዐላማ የእግዚአብሔርን ሕዝብ ከሚመጣው ቍጣ ለመጠበቅ ነው:: የዚህን ዳራ ለማወቅ ሕዝ 9፥4 ይመ:: ምልክቱ፣ "ታው" የተባለ የዕብራይስጥ ፊደል ሲሆን የአማርኛውን "ተ" ይመስላል::

7፥4 *መቶ አርባ አራት ሺሁ፤* አንዳንድ ሊቃውንት እዚህ ላይ የተጠቀሰው ቍጥር እውነተኞቹን የአይሁድ ነገዶች ማለትም፣ "ከታላቁ መከራ" (ቍ 14) የተረፉትን ታማኝ የአይሁድ ቅሬታዎችን ያመለክታል ይላሉ፤ ሌሎች ደግሞ ክፍሉ የሚያመለክተው በታላቁ መከራ ዘመን የሚኖሩትን ታማኝ አማኞችን በሙሉ ነው ይላሉ::

7፥5 *ከይሁዳ፤* ከታላቁ ወንድም ከሮቤል በፊት ስሙ የተጠቀሰው፣ መሲሑ የመጣው ከይሁዳ ወገን በመሆኑ ሊሆን ይችላል (ይሁንና የዘፍ 37፥21 ማብ ይመ)::

7፥6 *ምናሴ፤* ከሁለቱ የዮሴፍ ነገዶች አንዱ (ኤፍሬምና ምናሴ) ሲሆን፣ ስሙ ግን ለብቻው ተጠቅሷል፤ ይህም የሆነው የዳን ስም ስላልተጠቀሰ የነገዶቹን ቍጥር 12 ለማድረስ ሊሆን ይችላል:: የዳን ስም ያልተጠቀሰው ከጣዖት አምልኮ ጋር ስለ ተባበረ (መሳ18፥30) ወይም የክርስቶስ ተቃዋሚ የሚመጣው ከዚህ ነገድ ነው ተብሎ ስለሚታመን ሊሆን ይችላል::

7፥9 *ማንም ሊቈጥራቸው የማይችል፤* በቍ14 ላይ ከታላቁ መከራ የመጣው ሕዝብ እንደ ሆነ ተገልጾአል:: *ከሕዝብ፣ ከነገድ፣ ከወገን፣ ከቋንቋም ሁሉ፤* አራቱም በአንድነት በ5፥9፤ 11፥9፤ 13፥7፤14፥6 ላይ ተጠቅሰዋል:: ይሁንና ከአራቱ አንዱ መለወጡን በ10፥11፤17፥15 ላይ ይመ:: *የዘንባባ ዝንጣፊ፤* ለክብር በዓላት ማድመቂያ ያገለግላል (ዘሌ 23፥40፤ ዮሐ12፥13 ይመ)::

7፥10 *ማዳን ... የአምላካችን ... ነው፤* ዘፍ 49፥18 ("ማዳንህና")፤ ዮና 2፥9 ይመ::

7፥11 *በሽማግሌዎቹ፤* የ4፥4 ማብ ይመ:: *በአራቱም ሕያ*

ቆመው ነበር፤ በዙፋኑ ፊት በግንባራቸው ተደፍተው ለእግዚአብሔር ሰገዱ፤ [12]እንዲህም ይሉ ነበር፤

"አሜን፤
ውዳሴና ክብር፣
ጥበብ፣ ምስጋናና፣ ሞገስ፣
ኀይልና ብርታትም፣
ከዘላለም እስከ ዘላለም ድረስ ለአምላካችን
ይሁን፤
አሜን።"

[13]ከዚያም ከሽማግሌዎቹ አንዱ፣ "እነዚህ ነጭ ልብስ የለበሱት እነማን ናቸው? ከወዴትስ መጡ?" አለኝ።

[14]እኔም፣ "ጌታ ሆይ፤ አንተ ታውቃለህ" አልሁት።

እርሱም እንዲህ አለኝ፤ እነዚህ ከታላቁ መከራ የመጡ ናቸው፤ ልብሳቸውንም በበጉ ደም አጥበው "አንጽተዋል። [15]ስለዚህ፣

"በእግዚአብሔር ዙፋን ፊት ሆነው፣
ቀንና ሌሊት በመቅደሱ ያገለግሉታል፤
በዙፋኑም ላይ የተቀመጠው ድንኳኑን
በላያቸው ይዘረጋል፤
[16]ከእንግዲህ ወዲህ አይራቡም፤
ከዚህም በኋላ አይጠሙም፤
ፀሓይ አይመታቸውም፤
ሐሩሩም ሁሉ አያቃጥላቸውም፤
[17]ምክንያቱም በዙፋኑ መካከል ያለው በግ
እረኛቸው ይሆናል፤
ወደ ሕይወት ውሃ ምንጭም
ይመራቸዋል፤
እግዚአብሔር እንባን ሁሉ ከዐይናቸው
ያብሳል።"

7፥12 ሮሜ11፥36፤ ራእ5፥12-14
7፥13 ራእ3፥4
7፥14 ዕብ9፥14፤ 1ዮሐ1፥7፤ራእ12፥11፤ 22፥14
7፥15 ቍ9፤ኢሳ4፥5፡ 6፤ራእ5፥1፤11፥19፤ 21፥3፤22፥3
7፥16 ኢሳ49፥10፤ ዮሐ6፥35
7፥17 ኢሳ25፥8፤ 35፥10፤51፥11፤65፥19፤ ዮሐ4፥10፤10፥11፤ ራእ21፥4
8፥1 ራእ6፥1
8፥2 ቍ6-13፤ ማቴ24፥31፤ ራእ9፥1፡13፤11፥15
8፥3 ቍ5፤ዘፀ30፡ 1-6፤ዕብ9፥4፤ራእ5፥8፤ 7፥2፤9፥13
8፥4 መዝ141፥2
8፥5 ዘሌ16፥12፡13፤ ራእ4፥5፤6፥12
8፥6 ቍ2
8፥7 ቍ2፡7-12፤ ሕዝ38፥22፤ራእ9፥4፡ 15፡18፤12፥4
8፥8 ቍ7፤ኤር51፥25፤ ራእ16፥3
8፥9 ቍ7
8፥10 ኢሳ14፥12፤ ራእ6፥13፤9፥1፤14፥7፤ 16፥4
8፥11 ቍ7፤ኤር9፥15፤ 23፥15

## ሰባተኛው ማኅተምና የወርቁ ጥና

**8** በጉ ሰባተኛውን ማኅተም በፈታ ጊዜ፣ ግማሽ ሰዓት ያህል በሰማይ ዝምታ ሆነ።

[2]ከዚያም በእግዚአብሔር ፊት የሚቆሙትን ሰባቱን መላእክት አየሁ፤ ሰባት መለከትም ተሰጣቸው።

[3]ሌላም መልአክ የወርቅ ጥና ይዞ መጣና በመሠዊያው አጠገብ ቆመ፤ እርሱም በዙፋኑ ፊት ባለው የወርቅ መሠዊያ ላይ ከቅዱሳን ጸሎት ሁሉ ጋር እንዲያቀርበው ብዙ ዕጣን ተሰጠው። [4]የዕጣኑም ጢስ ከቅዱሳኑ ጸሎት ጋር ከመልአኩ እጅ ወደ እግዚአብሔር ፊት ወጣ። [5]መልአኩም ጥናውን ይዞ የመሠዊያውን እሳት ሞላበትና ወደ ምድር ወረወረው፤ ነጐድጓድ፣ ድምፅ፣ መብረቅና የምድር መናወጥ ሆነ።

## ሰባቱ መለከቶች

[6]ከዚያም ሰባቱን መለከት የያዙት ሰባቱ መላእክት ለመንፋት ተዘጋጁ።

[7]የመጀመሪያው መልአክ መለከቱን ነፋ፤ ደም የተቀላቀለበት በረዶና እሳት ወደ ምድር ተጣለ፤ የምድር አንድ ሦስተኛ ተቃጠለ፤ የዛፎችም አንድ ሦስተኛ ተቃጠለ፤ የለመለመውም ሣር ሁሉ ተቃጠለ።

[8]ሁለተኛውም መልአክ መለከቱን ነፋ፤ ትልቅ ተራራ የሚመስል ነገር በእሳት እየተቀጣጠለ ወደ ባሕር ተጣለ፤ የባሕሩ አንድ ሦስተኛ ወደ ደም ተለወጠ፤ [9]በባሕሩም ውስጥ ከሚኖሩት ሕያዋን ፍጡራን አንድ ሦስተኛ ሞተ፤ የመርከቦችም አንድ ሦስተኛ ወደመ።

[10]ሦስተኛውም መልአክ መለከቱን ነፋ፤ እንደ ችቦ የሚነድ ታላቅ ኮከብ በወንዞች አንድ ሦስተኛና በውሃ ምንጮች ላይ ከሰማይ ወደቀ፤ [11]የኮከቡም ስም "እሬቶ[a]" ይባል ነበር። የውሃውም አንድ ሦስተኛ መራራ ሆነ፤ ውሃው መራራ ከመሆኑ የተነሣም ብዙ ሰዎች ሞቱ።

[a]11 *ምሬት* ማለት ነው።

*ዋን ፍጡራን፤* የ4፥6 ማብ ይመ፡

7፥12 *ውዳሴና ... ብርታትም፤* እነዚህ ሰባት የውዳሴ ቃላት ሙሉነትንና ፍጹምነትን የሚገልጹ ናቸው (የ5፥12 ማብ ይመ)።

7፥13 *ነጭ ልብስ፤* የ6፥11 ማብ ይመ።

7፥14 *ከታላቁ መከራ፤* ክርስቶስ ዳግም ከመምጣቱ በፊት የሚሆነውን የመጨረሻውን የጠላትነት ዘመን ነው፤ አንዳንዶች የዚህን ጠላትነት መጀመሪያ በዮሐንስ ዘመን የነበረችው ቤተ ክርስቲያን አይታዋለች ይላሉ።

7፥15 *በመቅደሱ፤* በራእየ ዮሐንስ ውስጥ፣ "መቅደስ" የሚለው ቃል 16 ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን ሁሉም የሚያመለክቱት የመቅደሱን ውጫዊ ነገር ሳይሆን ውስጣዊ ነገር ነው። የእግዚአብሔር ህልዎት ወይም መገኘት የሚያድረው በዚህ ስፍራ ነው። *ድንኳኑን ... ይዘረጋል፤* በምድረ በዳ የነበረችውን የመገናኛ ድንኳን እንድናስታውስና (ዘሌ26፥11-13) የእግዚአብሔርን የክብር መገለጥ እንድናስብ የሚያደርግ ነው።

7፥17 *እረኛቸው፤* በጥንት ዘመን የነበሩ ነገሥታት ራሳቸውን የሕዝብ እረኛ አድርገው ይመለከቱ ነበር።

8፥1 *በሰማይ ዝምታ፤* ቀጥሎ የሚመጡት ተከታታይ መቅሠፍቶች ከመውረዳቸው በፊት ለጥቂት ጊዜ የቆየ ሕያውና አስደናቂ ጸጥታ ነው፤ እዚህ ላይ እንደምናየው የተውኔቱ የመጨረሻ ክፍል ከጥቂት ጊዜ በኋላ እንዲታይ ተደርጓል።

8፥2 *ሰባት መለከትም፤* በብሉይ ኪዳን ዘመን መለከት የሚነፋው በክብረ በዓላትና በጦርነት ጊዜ ነው። በራእ8-9፤ 11፥15-19 የምናገኛቸው ሰባቱ መለከቶች ተከታታይ መቅሠፍቶች እንደሚወርዱ የሚያውጁ ናቸው፤ የሚወርዱት መቅሠፍቶች ማኅተሞቹ በተከፈቱ ጊዜ ከወረዱት መቅሠፍቶች የበረቱ ቢሆኑም፣ እንደ ጽዋዎቹ ዶጋ ዐመድ የሚያደርጉ ግን አይደሉም (ም 16)።

8፥3 *ጥና፤* ፍም መያዣና ዕጣን ማጠኛ ነው (ከዘፀ 27፥3፤ 1ነገ 7፥50 ጋር ያነጻጽሩ)። *ከቅዱሳን ጸሎት ሁሉ ጋር፤* በርካታ ትርጕሞች ዕጣኑ ከጸሎት "ጋር" እንደሚቀላቀል ይናገራሉ። ይህን ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ሐረግ፣ ዕጣኑ ራሱ "ጸሎት እንደሆነ" ሊያመለክት ይችላል ("ጸሎት ያለበት ብዙ ዕጣን ተሰጠው")።

8፥4፤ ምንም እንኳ መላእክት የቅዱሳንን ጸሎት እግዚአብሔር ፊት ቢያቀርቡም፣ ጸሎቱ ተቀባይነት እንዲያገኝ ማድረግ አይችሉም። በአይሁድ አቡቀለምሲሳዊ ጽሑፎች ውስጥ መላእክት መካከለኛ መሆን ይችላሉ (በእግዚአብሔርና በሰው መካከል አማላጅ መሆን ይችላሉ) የሚለው የአይሁድ አሳብ በአዲስ ኪዳን ውስጥ ስፍራ የለውም።

8፥5 *ነጐድጓድ... የምድር መናወጥ፤* የ4፥5 ማብ ይመ።

8፥7 *ደም የተቀላቀለበት በረዶና እሳት፤* በግብፅ ላይ ከወረደው ከሰባተኛው መቅሠፍት ጋር ያነጻጽሩ (ዘፀ9፥13-25፤ ከሕዝ 38፥22 ጋር ያነጻጽሩ)። *የምድር አንድ ሦስተኛ ተቃጠለ፤* ይህ ክፍልፋይ እንደሚያመለክተው፣ በመለከቱ መነፋት የታወጀው ቅጣት ፍጹምና የመጨረሻ አይደለም (ቀጥለው ባሉት ሦስት መቅሠፍቶች ተመሳሳይ ክፍልፋይ ይታያል፤ ቍ 8-9፡10-11፡12)።

8፥8 *የባሕሩ ... ወደ ደም ተለወጠ፤* በግብፅ ላይ የወረደውን የመጀመሪያውን መቅሠፍት የሚያስታውስ ነው (ዘፀ7፥20-21)። ይህ የሥነ-ፍጻሜ ፍርድ እንጂ ከእሳተ ገሞራ የተነሣ የሚከሰት የአካባቢ ብክለት አይደለም።

8፥10 *ታላቅ ኮከብ ... ወደቀ፤* የ6፥13፤ 9፥1 ማብ ይመ።

8፥11 *እሬቶ፤* እጅግ መራራ ጣዕም ያለው ተክል ነው (እግ

[12]አራተኛው መልአክ መለከቱን ነፋ፤ የብርሃናቸው አንድ ሦስተኛ ይጨልም ዘንድ፣ የፀሓይ አንድ ሦስተኛ፣ የጨረቃም አንድ ሦስተኛ፣ የከዋክብትም አንድ ሦስተኛ ተመታ፤ የቀንም አንድ ሦስተኛ፣ የሌሊቱም አንድ ሦስተኛ ብርሃን እንዳይሰጥ ተከለከለ።

[13]ከዚያም ተመለከትሁ፤ አንድ ንስር በሰማይ መካከል ይበር ነበር፤ በታላቅ ድምፅም፣ "የቀሩት ሦስቱ መላእክት መለከት ስለሚነፉ፣ በምድር ላይ ለሚኖሩት ወዮላቸው! ወዮላቸው! ወዮላቸው!" ሲል ሰማሁ።

**9** አምስተኛው መልአክ መለከቱን ነፋ፤ ከሰማይ ወደ ምድር የወደቀውን ኮከብ አየሁ፤ ኮከቡም የጥልቁ ጒድጓድ መክፈቻ ተሰጠው። [2]ጥልቁን ጒድጓድ በከፈተውም ጊዜ፣ ከውስጡ ከታላቅ እቶን እንደሚወጣ ያለ ጢስ ወጣ፤ ከጒድጓዱም በወጣው ጢስ ፀሓይና ሰማይ ጨለሙ። [3]ከጢሱም አንበጣች ወጥተው በምድር ላይ ወረዱ፤ እንደ ምድር ጊንጦች ሥልጣን ያለ ሥልጣን ተሰጣቸው። [4]እነርሱም የምድርን ሣር ወይም ማናቸውንም የለመለመ ተክል ወይም ዛፍ እንዳይጐዱ፣ ነገር ግን የእግዚአብሔር ማኅተም በግምባራቸው ላይ የሌለባቸውን ሰዎች ብቻ እንዲጐዱ ተነገራቸው፤ [5]እነርሱንም አምስት ወር ብቻ እንዲያሠቃዩአቸው እንጂ እንዲገድሏቸው ሥልጣን አልተሰጣቸውም፤ የሚሠቃዩትም ሥቃይ ጊንጥ ሰውን ሲነድፍ እንደሚሰማው ዐይነት ሥቃይ ነው። [6]በእነዚያ ቀኖች ሰዎች ሞትን ይፈልጋሉ፤ ነገር ግን አያገኙትም፤ ለመሞትም ይመኛሉ፤ ነገር ግን ሞት ከእነርሱ ይሸሻል።

[7]አንበጦቹ ለጦርነት የተዘጋጁ ፈረሶች ይመስሉ ነበር፤ በራሳቸውም ላይ የወርቅ አክሊል የመሰለ ነገር ደፍተዋል፤ ፊታቸውም የሰው ፊት ይመስል ነበር፤ [8]ጠጒራቸው የሴት ጠጒር፣ ጥርሳቸውም የአንበሳ ጥርስ ይመስል ነበር። [9]የብረት ጥሩር የሚመስል ጥሩር ነበራቸው፤ የክንፎቻቸውም ድምፅ ወደ ጦርነት የሚገሠግሡ የብዙ ፈረሶችና ሠረገሎች ድምፅ ይመስል ነበር። [10]እንደ ጊንጥም ያለ ጅራትና መንደፊያ ነበራቸው፤ ደግሞም ሰዎችን አምስት ወር የሚያሠቃዩበት ኀይል በጅራታቸው ላይ ነበር። [11]በላያቸው ንጉሥ ነበራቸው፤ እርሱም የጥልቁ ጒድጓድ መልአክ ነው፤ ስሙም በዕብራይስጥ "አብዶን"፣ በግሪክ ደግሞ "አጶልዮን"[+] ይባላል።

[12]የመጀመሪያው ወዮ ዐልፎአል፤ እነሆ፤ ከዚህ በኋላ ገና ሌላ ሁለት ወዮዎች ይመጣሉ።

[13]ስድስተኛው መልአክ መለከቱን ነፋ፤ በእግዚአብሔር ፊት ካለው በወርቅ ከተሠራው መሠዊያ ቀንዶች ድምፅ ሲመጣ[ǂ]

8፥12 ቍ7፤ ዘፀ10፥21-23፤ ሕዝ32፥7፤ ራእ6፥12፡13
8፥13 ራእ3፥10፤ 9፥12፤11፥14፤12፥12፤ 14፥6፤19፥17
9፥1 ቍ2:11፤ ቍ8፥31፤ራእ1፥18፤ 8፥10
9፥2 ቍ1:11፤ ዘፍ19፥28፤ዘፀ19፥18፤ ኢዩ2፥2:10፤ ሉቃ8፥31
9፥3 ቍ5:10፤ ዘፀ10፥12-15
9፥4 ራእ6፥6፤7፥2: 3፤8፥7
9፥5 ቍ3:10
9፥6 ኢዮ3፥21፤ 7፥15፤ኤር8፥3፤ ራእ6፥16
9፥7 ናሆ7፥8፤ኢዩ2፥4
9፥8 ኢዩ1፥6
9፥9 ኢዩ2፥5
9፥10 ቍ3:5:19
9፥11 ቍ1:2: ኢዮ26፥6፤28፥22፤ 31፥12፤መዝ88፥11፤ ሉቃ8፥31፤ራእ16፥16
9፥12 ራእ8፥13
9፥13 ዘፀ30፥1-3፤ ራዕ8፥3

[+]11 አብዶን ወይም አጶልዮን ትርጒሙ አጥፊ ማለት ነው።
[ǂ]13 ሲወጣ ማለት ነው።

ራጭ ትርጒሙን ይመ)። እዚህ ላይ ተምሳሌታዊ በሆነ መንገድ የገባው መዐቱንና ሐዘኑን ለመግለጽ ነው (ምሳ5፥3-4፤ ኤር9፥15፤ ሰቆ 3፥19 ይመ)። ተክሉ መርዝነት የለውም፤ ሆኖም መራራነቱ የሚያመለክተው ሞትን ነው። *የውሃው ... መራራ ሆነ፤* በቃና ዘገሊላ ከተደረገው ታምር የተለየ ነው፤ በዚያ ውሃው ጣፋጭ ሆነ (ዘፀ 15፥25)።

8፥12 *የፀሓይ አንድ ሦስተኛ... ተመታ፤* በግብፅ ላይ የወረደው ዘጠነኛው መቅሠፍት ምድር ለሦስት ቀናት ያህል በድቅድቅ ጨለማ እንድትሸፈን አድርጎአል (ዘፀ 10፥21-23)። በግብፃውያን ላይ የወረደውን መቅሠፍት የሚያመለክተን፣ በራእየ ዮሐንስ ውስጥ የእግዚአብሔር ሕዝቦች በክፉ ኀይሎች ቍጥጥር ሥር ካለው ዓለም ባርነት ነጻ የሚወጡበት የመጨረሻ፣ "ውጽአት" ገና የሚቀር መሆኑን ነው።

8፥13 *ወዮላቸው! ወዮላቸው! ወዮላቸው!* እነዚህ ሦስት ወዮዎች ከመጨረሻዎቹ ሦስት መቅሠፍቶች ጋር ይዛመዳሉ (9፥12፤ 11፥14 ይመ)፤ ም10፥1-11፥13 ስረዋጽ ወይም መሀል ገብ ሐሳብ ነው፤ በም 15-16 ላይ የምናገኛቸው የሰባቱ ጽዋዎች ፍርድ ሦስተኛው ወዮ ናቸው። ወዮዎቹ የሚወርዱት በጻድቃን ላይ ሳይሆን (9፥4 ይመ) በማያምነው ዓለም ላይ ነው። ("በምድር ላይ ለሚኖሩት" የሚለው ሐረግ የሚያመለክተው ክፉዎቹን ነው፤ የ6፥10 ማብ ይመ)።

9፥1 *ከሰማይ ወደ ምድር የወደቀውን ኮከብ፤* በ8፥10 ላይ የተጠቀሰው ኮከብ በመላው ዓለም ላይ ከሚወርደው መቅሠፍት ጋር የተያያዘ ነበር፤ እዚህ ላይ የተጠቀሰው ኮኮብ ግን የመለኮት ወኪል ምናልባትም መልአክ ሊሆን ይችላል (ከ20፥1 ጋር ያነጻጽሩ)። *የጥልቁ ጒድጓድ፤* ከምድር በታች ያለ የአጋንንት መንጋ መናኸሪያ እንደ ሆነ ይነገራል (20፥1፤ ሉቃ 8፥31 ይመ)። ይህን ሐረግ ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል፣ "እጅግ ጥልቅ" ወይም፣ "መጨረሻ የሌለው" የሚል ትርጒም ያለው ሲሆን፣ የሰብዓ ሊቃናት ትርጒም (ከዕብራይስጥ ወደ ግሪክ ቋንቋ የተመለሰው ትርጒም) ይህን ቃል የተጠቀመበት በዕብራይስጥ፣ "የጥንቱ ጥልቅ" የሚለ ውን ለመግለጽ ነው (ዘፍ1፥2፤7፥11፤ ምሳ8፥28 ይመ)። ቃሉ በአዲስ ኪዳን ውስጥ የተጠቀሰው ዘጠኝ ጊዜ ሲሆን፣ ሰባቱ የሚገኘው በራእየ ዮሐንስ ውስጥ ነው።

9፥3 *አንበጣዎች፤* ዳራውን በተመለከተ በዘፀ 10፥1-20 ላይ ስለ አንበጣው መቅሠፍት የተነገረውን ይመ። ኢዩ1፥2-2፥11 የአንበጣዎቹን መቅሠፍት የሚተረጒመው የጌታ ቀን ሲመጣ ከሚከሰተው ታላቅ ጥፋት ጋር አያይዞ ነው። አንበጣ የሚጓዘው በመንጋ ሲሆን በአንድ ጊዜ በብዙ ሺህ ሄክታር መሬት ላይ የሚገኘውን ማንኛውንም ዕፅዋት ማውደም ይችላል። በ1866 ዓ.ም. በአልጀርስ የአንበጣ መንጋ ባስከተለው መቅሠፍት 200,000 ሰዎች በረሃብ አልቀዋል። *ጊንጦች፤* ሸረሪት የሚመስል ፍጥረት ሲሆን፣ በጅራቱ ጫፍ ላይ የሚጐዳ ወይም የሚገድል መርዝ አለው።

9፥4 *የእግዚአብሔር ማኅተም ... የሌለባቸውን ሰዎች፤* የመጀመሪያው ወዮ፣ "የእግዚአብሔርን አገልጋዮች" አይጐዳም (7፥3 ይመ)። በግብፃውያን ላይ ከወረደው መቅሠፍት ከተጠበቁት እስራኤላውያን ጋር ያነጻጽሩ (ዘጸ 8፥22፤ 9፥4:26፤ 10፥23፤ 11፥7)።

9፥5 *አምስት ወር፤* የአንበጣን ዑደተ ሕይወት ወይም የበጋውን ወራት የሚጠቁም የተወሰነ ወቅት ነው፤ በዚህ ወቅት የአንበጣ መንጋ መከሠቱ የማይቀር ነው።

9፥6 *ሞትን ይፈልጋሉ፤ ነገር ግን አያገኙትም፤* ከሆሴ 10፥8 ጋር ያነጻጽሩ (በሉቃ 23፥30 ላይ ተጠቅሶአል)። ከክርስቶስ ልደት በፊት በመጀመሪያው ምእተ ዓመት ይኖር የነበረው ቆርኔሌዎስ ጋለስ የተባለ የሮም ባለቅኔ፣ "ከቍስል ሁሉ እጅግ የሚከፋው፣ ሞትን ፈልጎ አለማግኘት ነው" ብሎ ነበር። በፊል1፥23-24 ላይ ጳውሎስ ስለ ሞት ከነበረው አመለካከት ጋር ያነጻጽሩ።

9፥7 *የሰው ፊት፤* አንበጣዎቹ የአውሬነት ብቻ ሳይሆን እንደ ሰው የመሰሪነት ባሕርይ ነበራቸው።

9፥8 *የሴት ጠጒር፤* ምናልባት የአንበጣዎቹን ረጃጅም አንቴና ሊሆን ይችላል። *የአንበሳ ጥርስ፤* ጭካኔንና ኢሰብዓውዊነትን ለመግለጽ ነው።

9፥9 *የብረት ጥሩር የሚመስል* በቆዳ ላይ የተሰፋ የብረት መከላከያ ሳይሆን አይቀርም *ጥሩር፤* የጥንት ወታደሮች በውጊያ ላይ የሚለብሱት ከብረት የተሠራ የብረት መከላከያ ነው።

9፥10 *አምስት ወር፤* የቍ 5 ማብ ይመ።

9፥11 *አብዶን፤* የጥፋት ምሳሌ ነው። አግራጭ ትርጒሙን ይመ፤ ከምሳ 15፥11 ጋር ያነጻጽሩ።

9፥12 *የመጀመሪያው ወዮ፤* የ8፥13 ማብ ይመ።

9፥13 *በወርቅ ከተሠራው መሠዊያ ቀንዶች፤* 8፥3-5 ይመ። ቀንዶቹ የሚገኙት በመሠዊያው በአራቱም ማእዘን ጫፎች ላይ

ሰማሁ፤ [14]ድምፁም መለከት የያዘውን ስድስተኛውን መልአክ፣ "በታላቁ ወንዝ በኤፍራጥስ የታሰሩትን አራቱን መላእክት ፍታቸው" አለው። [15]ከሰው ዘር አንድ ሦስተኛውን እንዲገድሉ፣ ለዚህች ሰዓትና ዕለት እንዲሁም ለዚህች ወርና ዓመት ተዘጋጅተው የነበሩት አራቱ መላእክት ተፈቱ። [16]የፈረሰኛው ሰራዊት ብዛት ሁለት መቶ ሚሊዮን ነበር፤ ቍጥራቸውንም ሰማሁ።

[17]በራእዬ ያየኋቸው ፈረሶችና በላያቸው የተቀመጡት ይህን ይመስሉ ነበር፤ ጥሩራቸው እንደ እሳት ቀይ፣ እንደ ያክንት ሰማያዊና እንደ ዲን ብጫ ነበር፤ የፈረሶቹ ራስ የአንበሶችን ራስ ይመስል ነበር። ከአፋቸውም እሳትና ጢስ፣ ዲንም ይወጣ ነበር። [18]ከአፋቸው በወጡት፣ በሦስቱ መቅሠፍቶች፣ ማለት በእሳቱ፣ በጢሱና በዲኑ አንድ ሦስተኛው የሰው ዘር ተገደለ። [19]ምክንያቱም የፈረሶቹ ኀይል በአፋቸውና በጅራታቸው ላይ ነበር፤ ጅራታቸውም እባብ ይመስል ነበር፤ ራስ ስላላቸው ጕዳት የሚያደርሱት በእርሱ ነበር።

[20]በእነዚህ መቅሠፍቶች ሳይገደሉ የቀሩት ሰዎች አሁንም ከእጃቸው ሥራ ንስሓ አልገቡም፤ አጋንንትን እንዲሁም ማየት ወይም መስማት ወይም መሄድ የማይችሉትን፣ ከወርቅ፣ ከብር፣ ከናስ፣ ከድንጋይና ከዕንጨት የተሠሩትን ጣዖቶች ማምለክ አልተዉም፤ [21]ደግሞም ከነፍስ ግድያቸው፣ ከጥንቈላ ሥራቸው፣ ከዝሙት ርኵሰታቸው ወይም ከስርቆት ተግባራቸው ንስሓ አልገቡም።

## መልአኩና ትንሿ መጽሐፍ

**10** ከዚህ በኋላ ሌላ ብርቱ መልአክ ደመና ተጐናጽፎ ከሰማይ ሲወርድ አየሁ፤ እርሱም በራሱ ላይ ቀስተ ደመና ነበር። ፊቱ እንደ ፀሓይ፣ እግሮቹ እንደ እሳት ዐምዶች ነበሩ። [2]በእጁም የተከፈተች ትንሽ ጥቅልል መጽሐፍ ይዞ ነበር፤ ቀኝ እግሩን በባሕር ላይ፣ ግራ እግሩን በምድር ላይ አኖረ፤ [3]እንደሚያገሣ አንበሳም ድምፁን ከፍ አድርጎ ጮኸ፤ በጮኸም ጊዜ የሰባቱ ነጐድጓዶች ድምፆች ተናገሩ። [4]ሰባቱ ነጐድጓዶች በተናገሩ ጊዜ፣ ለመጻፍ ተዘጋጀሁ፤ ነገር ግን፣ "ሰባቱ ነጐድጓዶች የተናገሩትን በማኅተም ዝጋው እንጂ አትጻፍ" የሚል ድምፅ ከሰማይ ሰማሁ።

[5]ከዚህ በኋላ በባሕርና በምድር ላይ ቆሞ ያየሁት መልአክ ቀኝ እጁን ወደ ሰማይ አነሣ፤ [6]እርሱም ከዘላለም እስከ ዘላለም በሚኖረው፣ ሰማይንና በውስጡ ያሉትን፣ ምድርንና በውስጧ ያሉትን፣ ባሕርንና በውስጡ ያሉትን በፈጠረው በእርሱ ማለ፤ እንዲህም አለ፤ "ከእንግዲህ መዘግየት አይኖርም፤ [7]ነገር ግን ሰባተኛው መልአክ መለከቱን በሚነፋባቸው ቀኖች፣ ለአገልጋዮቹ ለነቢያት በገለጠላቸው መሠረት የእግዚአ

9፥14 ዘፍ15፥18፤ ዘዳ1፥7፤ ኢሱ1፥4፤ ኢሳ11፥15፤ ራእ11፥15፤ ራእ7፥1፤ 16፥12
9፥15 ቍ18፤ ራእ 8፥7፤ 20፥7
9፥16 ራእ5፥11፤ 7፥4
9፥17 ቍ18፤ መዝ11፥6፤ ኢሳ30፥33፤ ሕዝ38፥22፤ ራእ11፥5፤ 14፥10፤ 19፥20፤ 20፥10፤ 21፥8
9፥18 ቍ15፡17፤ ራእ8፥7
9፥20 ዘዳ4፥28፤ 31፥29፤ መዝ115፥4-7፤ 135፥15-17፤ ኢር1፥16፤ ዳን5፥23፤ ሚክ5፥13፤ ሐሥ7፥41፤ 1ቆሮ10፥20
9፥21 ኢሳ47፥9፡12፤ ራእ2፥21፤ 17፥2፡5፤ 18፥23
10፥1 ሕዝ1፥28፤ ማቴ17፥2፤ ራእ1፥15፡ 16፤ 4፥3፤ 5፥2፤ 18፥11 20፥1
10፥2 ቍ5፡8-10፤ ራእ5፥1
10፥3 ሆሴ11፥10፤ ራእ4፥5
10፥4 ቍ8፤ ዳን8፥26፤ 12፥4፡9፤ ራእ1፥11፡ 19፤ 22፥10
10፥5 ቍ1፡2፤ ዘጸ32፥40፤ ዳን12፥7
10፥6 ዘፍ14፥22፤ ዘፀ6፥8፤ ዘኍ14፥30፤ መዝ115፥15፤ 146፥6፤ ራእ1፥18፤ 4፥11፤ 14፥7፤ 16፥17

ነው (ዘፀ 27፥2)። ከፍርድ የሚሸሹ ሰዎች ሮጠው የመሠዊያውን ቀንድ ከያዙ ከፍርዱ ያመልጣሉ (1ነገ 1፥50-51፤ 2፥28፤ የአሞ 3፥14 ማብ ይመ)።

9፥14 *ኤፍራጥስ፤* በምዕራብ እስያ የሚገኝ ረጅሙ ወንዝ ነው (ርዝመቱ 2,735 ኪሎ ሜትር ያህል ይሆናል)። ወንዙ እስራኤልን በስተ ምሥራቅ ካሉት ታሪካዊ ጠላቶቿ (አሦርና ባቢሎን) የሚያዋስን ነው (ከኢሳ8፥5-8 ጋር ያነጻጽሩ)። *አራቱን መላእክት፤* በአጋንንት የሚመሩትን ፈረሰኞች የሚቈጣጠሩ ሊሆኑ ይችላሉ (ቍ15-19)።

9፥15 *ሰዓትና ... ዕለት ... ወርና ... ዓመት፤* በአቡቀለምሲሳዊ እሳቤ መሠረት፣ እግዚአብሔር ፈቃዱን የሚያከናውነው እርሱ ራሱ ለይቶ በወሰነው የጊዜ ሠሌዳ መሠረት ነው።

9፥16 *ሁለት መቶ ሚሊዮን፤* እዚህ ላይ የተጠቀሰው አኀዝ ጥቅል ነው፤ ይህም የሰራዊቱ ቍጥር እጅግ ከፍተኛ መሆኑን እንጂ የተወሰነ ቍጥር ያለው መሆኑን ለመግለጽ አይደለም (ከመዝ 68፥17፤ ዳን7፥10፤ ራእ5፥11 ጋር ያነጻጽሩ)።

9፥17 *ጥሩራቸው፤* የቍ 9 ማብ ይመ። *ከአፋቸውም እሳት ... ይወጣ ነበር፤* በ11፥5 ላይ ካሉት ሁለት ምስክሮች ጋር ያነጻጽሩ።

9፥19 *ጅራታቸውም እባብ ... ራስ ስላላቸው፤* የፈረሶቹ መገኛ አጋንንት እንደሆኑ አበክሮ የሚገልጽ ነው (ከ12፥9 ጋር ያነጻጽሩ)።

9፥20 *አጋንንትን፤* ከሰይጣን ጋር ተባብረው የሚሠሩና በሰዎች ጕዳይ ጣልቃ እየገቡ አሉታዊ ተጽእኖ የሚያሳድሩ መንፈሳዊ ፍጥረታት ናቸው (ከዘዳ4፥28፤ መዝ115፥5-7፤ 1ቆሮ10፥20 ጋር ያነጻጽሩ)።

9፥21 *ንስሓ አልገቡም፤* 16፥9፡11 ይመ። በአካል ላይ የሚደርሰው መከራ እንኳ የሰዎችን ዐመፀኛ ልብ መለወጥ አልቻለም። *ከጥንቈላ ሥራቸው፤* ለጥንቈላ ሥራቸው ሥር የሚምሱና ቅጠል የሚበጥሱ አስማተኞችና መተተኞች ናቸው (ይህን ለመግለጽ የገባው የግሪኩ ቃል፣ "ፋርማኪን" የሚል ሲሆን፣ "ፋርማሲ" (መድኀኒት ቤት የሚለው የእንግሊዝኛ ቃል የመጣውም ከዚሁ ቃል ነው)። በኤፌሶን ይኖሩ የነበሩ አማኞቹ 50,000 ድራክማስ የሚያወጣውን የጥንቈላ መጻሕፍቶቻቸውን በአደባባይ አቃጠሉ (ሐሥ9፥19)።

10፥1 *ብርቱ መልአክ፤* ምናልባት በ5፥2 ላይ የተጠቀሰው መልአክ ሊሆን ይችላል። *ቀስተ ደመና፤* ከሕዝ1፥26-28 ጋር ያነጻጽሩ። ቀስተ ደመና እግዚአብሔር ምድርን እንደ ገና በውሃ እንደማያጠፋት ቃል ኪዳን የገባበት ምልክት ነው (ዘፍ 9፥8-17)። *እግሮቹም እንደ እሳት ዐምዶች ነበሩ፤* ለዚህ ለራእየ ዮሐንስ ማእከላዊ ክፍል እንደ ዳራ የሚያገለግለው የዘፀአት መጽሐፍ በመሆኑ (የ8፥12 ማብ ይመ)፣ ይህ ሐረግ የሚያመለክተው እስራኤላውያን በምድረ በዳ ይጓዙ በነበረበት ሰዓት ይመራቸውና (ዘፀ13፥21-22) ይጠብቃቸው (ዘፀ14፥19፡24) የነበረውን የእሳትና የደመና ዐምድ ነው።

10፥2 *ትንሽ ጥቅልል መጽሐፍ፤* በም5 ላይ እንደተገለጸው ዐይነት ጥቅልል መጽሐፍ አይደለም፤ ምክንያቱም ያ ጥቅልል መጽሐፍ የተዘጋጀው በውስጡ የያዘውን ለመግለጥ ሲሆን ይህ ግን እንዲበላ ነው። ከዚህም በላይ፣ "ትንሽ ጥቅልል መጽሐፍ" የሚለው ሐረግ ይህንን ጥቅልል መጽሐፍ ከሌሎቹ መጻሕፍት የተለየ ያደርገዋል። *ቀኝ እግሩን በባሕር ላይ፣ ግራ እግሩንም በምድር ላይ፤* ግዙፍ ፍጡር መሆኑንና የእርሱ መምጣት የፍጥረትን ሁሉ ዕድል ፈንታ የሚወስን መሆኑ የሚያሳይ አገላለጽ ነው (ከቍ6 ጋር ያነጻጽሩ)።

10፥3 *የሰባቱ ነጐድጓዶች፤* በ8፥5፤ 11፥19፤ 16፥18 ላይ ነጐድጓድ የተያያዘው ከመለኮታዊ ቅጣት ጋር ነው። እዚህም ላይ ቢሆን ቃሉ የሚያመለክተው የእግዚአብሔርን ፍቅርና ጸጋ በማይቀበሉት ላይ ፍርድ የሚመጣባቸው መሆኑን ነው።

10፥4 *በማኅተም ዝጋው፤* በዳን 8፥26፤ 12፥4፡9 ላይ የተጠቀሱት ትንቢቶች በመጨረሻው ዘመን እስከሚከፈቱበት ጊዜ ድረስ ተዘግተዋል። ሰባቱ ነጐድጓዶች የተናገሩት ነገር ከትክክለኛው ጊዜ በፊት አይከፈትም። በ22፥10 ላይ የራእየ ዮሐንስን ትንቢቶች እንዳያትመው ከታዘዘው መልአክ ጋር ያነጻጽሩ፡

10፥5 *ቀኝ እጁን... አነሣ፤* መሐላ ሲደረግ ነገሩ የሚጸናው በዚህ ዐይነት ነው (ዘፍ 14፥22-23፤ ዘዳ32፥40 ይመ)።

10፥6 *ከዘላለም እስከ ዘላለም በሚኖረው፤* በቅርቡ ብዙ ሰማዕትነት እንደሚኖር በተነገረበት ዐውድ ውስጥ ብርቱ የማጽናኛ ቃል ነው (ከ1፥18፤ 4፥9-10፤ 15፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። *መዘግየት አይኖርም፤* በ6፥9-11 የተጠቀሱት ሰማዕታት ለጥቂት ጊዜ እንዲያርፉ ተነግሮአቸዋል፤ ይሁን እንጂ አሁን ፍጻሜው ደርሶአል (ከዳን 12፥1፤ ማር 13፥19 ጋር ያነጻጽሩ)።

10፥7 *የእግዚአብሔር ምስጢር፤* በአቡቀለምሲሳዊ እሳቤ

ብሔር ምስጢር ይፈጸማል።"

[8]ከዚያም ከሰማይ የሰማሁት ድምፅ እንደ ገና እንዲህ ሲል ተናገረኝ፣ "ሂድ፤ በባሕርና በምድር ላይ ከቆመው መልአክ እጅ የተከፈተችውን ጥቅልል መጽሐፍ ውሰድ።"

[9]እኔም ወደ መልአኩ ሄጄ ትንሿን ጥቅልል መጽሐፍ እንዲሰጠኝ ጠየቅሁት፤ እርሱም፣ "ውሰድና ብላት፤ ሆድህን መራራ ታደርገዋለች፤ በአፍህ ግን እንደ ማር ትጣፍጣለች" አለኝ። [10]ትንሿንም መጽሐፍ ከመልአኩ እጅ ተቀብዬ በላኋት፤ በአፌ እንደ ማር ጣፈጠች፤ ከበላኋት በኋላ ግን ሆዴ መራራ ሆነ፤ [11]ከዚያም፣ "ስለ ብዙ ሕዝቦች፣ ወገኖች፣ ቋንቋዎችና ነገሥታት እንደ ገና ትንቢት ልትናገር ይገባሃል" ተባልሁ።

## ሁለቱ ምስክሮች

**11** ከዚያም ሸምበቆ የመሰለ መለኪያ በትር ተሰጠኝ፤ እንዲህም ተባልሁ፤ "ሂደህ የእግዚአብሔርን ቤተ መቅደስና መሠዊያውን ለካ፤ በዚያም የሚያመልኩትን ቍጠር። [2]የውጭውን አደባባይ ግን ተወው፤ አትለካው፤ ለአሕዛብ የተሰጠ ነውና። እነርሱ የተቀደሰችውን ከተማ አርባ ሁለት ወር ይረግጧታል። [3]ለሁለቱ ምስክሮቼ ኀይል እሰጣቸዋለሁ፤ እነርሱም ማቅ ለብሰው አንድ ሺህ ሁለት መቶ ሥልሳ ቀን ትንቢት ይናገራሉ።" [4]እነዚህም በምድር ጌታ ፊት የሚቆሙት ሁለቱ የወይራ ዛፎችና ሁለቱ መቅረዞች ናቸው። [5]ማንም እነርሱን ሊጐዳ ቢፈልግ፣ እሳት ከአፋቸው ወጥቶ ጠላቶቻቸውን ያጠፋል፤ ሊጐዳቸው የሚፈልግ ሁሉ መሞት ያለበት በዚህ ዐይነት ነው። [6]እነዚህ ሰዎች ትንቢት በሚናገሩባቸው ወራት ዝናብ እንዳይዘንብ ሰማይን ለመዝጋት ሥልጣን አላቸው፤ ደግሞም ውሃዎችን ወደ ደም ለመለወጥ በሚፈልጉበት ጊዜ ሁሉ ምድርን በማንኛውም መቅሠፍት ለመምታት ሥልጣን አላቸው።

[7]ምስክርነታቸውን ከጨረሱ በኋላ ከጥልቁ የሚወጣው አውሬ ይዋጋቸዋል፤ ድል ይነሣቸዋል፤ ይገድላቸዋልም። [8]ሬሳቸውም በታላቂቱ ከተማ አደባባይ ይጣላል፤ ይህች ከተማ ሰዶምና ግብፅ እየተባለች በምሳሌ የምትጠራውና የእነርሱም ጌታ የተሰቀለባት ናት። [9]ከወገን፣ ከነገድ፣ ከቋንቋና ከሕዝብ የመጡ ሰዎች ሬሳቸውን ሦስት ቀን ተኩል ይመለከታሉ፤ ሬሳቸውም እንዳይቀበር ይከለክላሉ። [10]እነዚህ ሁለት ነቢያት የምድር ነዋሪዎችን ያሠቃዩ ስለ ነበር፣ በምድር የሚኖሩ ሰዎች በእነርሱ ላይ በደረሰው ደስ ይላቸዋል፤ እርስ በርሳቸውም

10፥7 አሞ3፥7ማቴ 24፥31፤ሮሜ16፥25
10፥8 ቍ2፡4
10፥9 ኤር15፥16፤ ሕዝ2፥8-3፡3
10፥10 ቍ9
10፥11 ሕዝ37፥4፡9፤ ዳን3፥4፤ራእ13፥7
11፥1 ሕዝ40፥3፤ ራእ21፥15
11፥2 ቍ3፤ ሕዝ40፥17፡20፤ ዳን7፥25፤12፥7፤ሉቃ 21፥24፤ራእ12፥6፡ 14፤13፥5፤21፥2
11፥3 ቍ2፤ዘፍ37፥34፤ 2ሳሙ3፥31፤ነህ9፥1፤ ዮና3፥5፤ራእ1፥5፤12፥13
11፥4 መዝ52፥8፤ ኤር11፡16፤ዘካ4፥3፡1 1፡14
11፥5 ዘኍ16፥29፡ 35፤2ሳሙ22፥9፤ 2ነገ1፥10፤ኤር5፡14፤ ራእ9፥17፡18
11፥6 ቍ3፤ዘፀ 7፥17፡19፤ሉቃ4፥25፤ ራእ8፥8
11፥7 ዳን7፥21፤ ሉቃ8፥31፤ራእ13፥1-4፡7
11፥8 ኢሳ1፥9፤ኤር 23፥14፤ሕዝ16፥46፤ዕብ 13፥12፤ራእ16፥19
11፥9 መዝ79፥2፡3፤ ራእ13፥7
11፥10 ነህ8፥10፡12፤

ውስጥ በሰማይ የተሰወሩ ምስጢራት ለባለ ራእዩ (ለአቡቀለምሲሱ አምጪ) ተገልጠዋል። እዚህ ላይ ምስጢሩ እግዚአብሔር የክፉ ኀይላትን ድል ማድረጉና ከዘላለም እስከ ዘላለም መንገሡ ነው (ከ11፥15 ጋር ያነጻጽሩ)።

10፥9 *ውሰድና ብላት*፤ የጥቅልሏን መጽሐፍ ሐሳብ በሚገባ አስተውል፤ አብላላ ማለት ነው (ከመዝ119፥103 ጋር ያነጻጽሩ)። *ሆድህን መራራ ታደርገዋለች*፤ የትንሿ ጥቅልል መጽሐፍ መልእክት (11፥1-13) ሥቃይን ወይም፣ "መጥፎ ወሬን" ያካትታል። *በአፍህ ግን እንደ ማር ትጣፍጣለች*፤ የእግዚአብሔር ዘላለማዊ ዕቅድ ማለትም፣ "መልካሙ ዜና" አይዘገይም።

10፥11 *እንደ ገና ትንቢት*፤ በ11፥15 ሰባተኛው መለከት ከተነፋ በኋላ የሚሆነውን ትንቢት ነው (የ7፥9 ማብ ይመ)።

11፥1 *ሸምበቆ*፤ በዮርዳኖስ ወንዝ ዳርቻ ችምችም ብሎ የሚበቅል ቀርከሃ መሰል ተክል ሲሆን፣ ቁመቱ እስከ 6ሜትር ይደርሳል። ሸምበቆ ቀጥ ያለና ቀላል በመሆኑ ለመለኪያ አመቺ ነው (ሕዝ40፥3፤ ዘካ2፥1-2 ይመ)። *ቤተ መቅደስና*፤ የ7፥15 ማብ ይመ። *መሠዊያውን*፤ በዚህ ዐውድ ውስጥ ስለ አምልኮ የተነገረ በመሆኑ፣ ምናልባት መሠዊያው ትልቅ ሳይሆን አይቀርም።

11፥2 *የውጭውን አደባባይ*፤ የአሕዛብ አደባባይ ሲሆን፣ ስፋቱ 10.5 ሄክታር ይሆናል ። *የተቀደሰችውን ከተማ...ይረግጧታል*፤ ከመዝ79፥1፤ ኢሳ63፥18፤ ሉቃ21፥24 ጋር ያነጻጽሩ። *አርባ ሁለት ወር*፤ ሦስት ዓመት ተኩል ነው። አንዳንዶች ይህን ዘመን ጨካኙ የሶርያ ንጉሥ አንትዮከስ ኤፒፋነስ (168-165 ዓ.ቅ.ክ) አይሁዶችን ያሠቃየበት ዘመን ነው ይላሉ። ሌሎች ደግሞ ምንም እንኳ ቤተ መቅደሱ በአንትዮከስ ለሦስት ዓመት ያህል ቢረገጥም፣ በራእየ ዮሐንስ ውስጥ የምናገኘው ሦስት ዓመት ተኩል የሚለው አነዝ የሚያመለክተው፣ "የሰባቱን ዓመት" እኩሌታ ነው (በዳን 9፥27) ይላሉ። ይህ ዘመን ወይም ጊዜ አንድ ሺህ ሁለት መቶ ሥልሳ ቀን (ቍ3፤12፥6) እንዲሁም "አንድ ዘመን፣ ዘመናትና የዘመናት እኩሌታ" ተብሎአል (12፥14፤ ከዳን 7፥25፤ 12፥7 ጋር ያነጻጽሩ)። ይህ ዘመን ለተወሰነ ጊዜ የሚሠለጥነውን ርኩሰት ለመግለጽ የሚያገለግል የተለመደ ትእምርት ነው።

11፥3 *ለሁለቱ ምስክሮቼ*፤ በሙሴና በኤልያስ ምሳሌ መሠረት ነው (የቍ 5-6 ማብ ይመ)። ምናልባት በመጨረሻው ዘመን ክርስቶስ ዳግም ከመምጣቱ በፊት በዓለም ሁሉ የሚመሰክሩትን አማኞች የሚወክሉ ናቸው። ወይም ደግሞ እውነትን ሲያበሥሩ ሰማዕት የሚሆኑ ሁለት ሰዎችን ሊሆን ይችላል። ወይም እውነትን ከማብሠራቸው የተነሣ ሰማዕት ሊሆኑ ስለሚችሉ ሁለት ሰዎች ሊሆን ይችላል። *ማቅ*፤ ከፍየል ወይም ከግመል ጠጕር የሚሠራ ጥቁር ሻካራ ልብስ ነው፤ የሚለበሰውም የሐዘንና የንስሐ ምልክት እንዲሆን ነው (ኢል1፥13፤ዮና3፥5-6፤ ማቴ 11፥21)። *አንድ ሺህ ሁለት መቶ ሥልሳ ቀን*፤ የቍ 2 ማብ ይመ፤ እነዚህ 30 ቀን ያላቸው ወራት ናቸው (42 ወራት X 30 ቀናት = 1,260 ቀናት )።

*11፥4*፤ እዚህ ላይ የቀረበው ምስል እንደሚያሳየው ፍሬያማ ምስክርነት መስጠት የሚቻለው በእግዚአብሔር መንፈስ አማካይነት ነው (የዘካ 4 ማብ ይመ)።

11፥5 *እሳት ወጥቶ ... ያጠፋል*፤ ኤልያስ ከአካዝያስ መልእክተኞች ጋር ያደረገውን ትግል ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (1ነገ 1፥10፡12)።

11፥6 *ሰማይን ለመዝጋት ሥልጣን አላቸው*፤ በኤልያስ ዘመን ከነበረው ድርቅ ጋር ያነጻጽሩ (1ነገ17፥1፤ ሉቃ4፥25፤ ያዕ 5፥17 ይመ)። *ውሃዎችን ወደ ደም*፤ እግዚአብሔር ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ መቅሠፍት በግብፃውያን ላይ እንዲያወርድ ሙሴን ተጠቅሞበታል (ዘፀ7፥17-21) ።

11፥7 *አውሬ*፤ በመጨረሻው ዘመን የእግዚአብሔርን ሕዝብ ከሚቃወሙት መካከል አንዱና ዋነኛው ነው (ም13፡17 ይመ)። ከጥልቁ መውጣቱ ደግሞ (የ9፥1 ማብ ይመ)፣ የአጋንንት ባሕርይ እንዳለው ያመለክታል። *ይገድላቸዋልም*፤ ልክ እንደ እነርሱ ጌታ ተመሳሳይ ነገር ይገጥማቸዋል (ቍ 8 ይመ)።

11፥8 *ሬሳቸውም ... አደባባይ ይጣላል*፤ በጥንት መካከለኛው ምሥራቅ የአንድን ሰው ሬሳ እንዳይቀበር መከልከል የሰውን ክቡርነት እንደ መናቅ ይቈጠራል። *በታላቂቱ ከተማ*፤ ምንም እንኳ አንዳንድ ሰዎች ሮም፣ ባቢሎን ወይም ሌላ ከተማ ናት ቢሉም ምናልባት ግን ኢየሩሳሌም ናት። እግዚአብሔርን ለሚቃወመው ዓለም ምልክት ናት (16፥19፤ 17፥18፤ 18፥10፡ 16፡18-19፡ 21 ይመ)። ሰዶም (ኢሳ1፥10 ይመ) የምግባረ ብልሹነት (ከዘፍ19፥4-11 ጋር ያነጻጽሩ)፣ ግብፅ ደግሞ የጭቈናና የባርነት ምሳሌ ናቸው። አንዳንድ ሊቃውንት ኢየሱስ ሮም ሊሰቀል ይችል ነበር ይላሉ፤ እንዲህ ሲሉ የሮም ግዛት አኔ በወቅቱ በሚታወቀው ዓለም ሁሉ ተንሰራፍቶ ስለ ነበር ለክርስቶስ ሞት ተጠያቂ የሚሆኑት እነርሱው ናቸው ማለታቸው ነው።

11፥9 *ሦስት ቀን ተኩል*፤ ከሦስት ቀን ተኩሉ አገልግሎታቸው ጋር ሲነጻጸር በጣም አጭር ጊዜ ነው። *ሬሳቸው እንዳይቀበር ይከለክላሉ*፤ የቍ8 ማብ ይመ።

ስጦታ ይለዋወጣሉ።

[11]ከሦስቱ ቀን ተኩል በኋላ ግን፣ የሕይወት እስትንፋስ ከእግዚአብሔር ዘንድ መጥቶ ገባባቸው፤ እነርሱም ተነሥተው በእግሮቻቸው ቆሙ፤ ይመለከቷቸውም በነበሩት ላይ ታላቅ ድንጋጤ ወረደባቸው። [12]ከዚያም፣ "ወደ ዚህ ውጡ!" የሚላቸውን ታላቅ ድምፅ ከሰማይ ሰሙ፤ ጠላቶቻቸው እየተመለከቷቸው በደመና ወደ ሰማይ ወጡ።

[13]በዚያም ሰዓት ታላቅ የምድር መናወጥ ሆነ፤ የከተማዪቱም አንድ ዐሥረኛ ወደመ፤ በነውጡም ሰባት ሺህ ሰዎች ሞቱ፤ የተረፉትንም ፍርሀት ያዛቸው፤ ለሰማይም አምላክ ክብር ሰጡ።

[14]ሁለተኛው ወዮ ዐልፎአል፤ እነሆ፤ ሦስተኛው ወዮ ቶሎ ይመጣል።

## ሰባተኛው መለከት

[15]ሰባተኛውም መልአክ መለከቱን ነፋ፤ በሰማይም እንዲህ የሚሉ ታላላቅ ድምፆች ተሰሙ፤

"የዓለም መንግሥት፣
የጌታችንና የእርሱ ክርስቶስ መንግሥት
ሆነች፤
እርሱም ከዘላለም እስከ ዘላለም
ይነግሣል።"

[16]በእግዚአብሔር ፊት በዙፋኖቻቸው ላይ የተቀመጡት ሃያ አራቱ ሽማግሌዎችም በግምባራቸው ተደፍተው ለእግዚአብሔር ሰገዱ፤ [17]እንዲህም አሉ፤

"ያለህና የነበርህ፣
ሁሉን ቻይ፤
ጌታ እግዚአብሔር ሆይ፤ እናመሰግንሃለን፤
ምክንያቱም አንተ ታላቁን ኀይልህን
ይዘህ ነግሠሃል።
[18]አሕዛብ ተቈጥተው ነበር፤
የአንተም ቍጣ መጣች፤
በሙታን ላይ የምትፈርድበት፣
ለአገልጋዮችህ ለነቢያት፣
ለቅዱሳንና ስምህን ለሚፈሩት፣
ለታናናሾችና ለታላላቆች ዋጋቸውን
የምትሰጥበት፣
ምድርንም ያጠፉትን የምታጠፋበት
ዘመን መጣ።"

[19]ከዚያም በሰማይ ያለው የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ ተከፈተ፤ በመቅደሱም ውስጥ የኪዳኑ ታቦት ታየ፤ መብረቅ፣ ድምፅ፣ ነጐድጓድ፣ የምድር መናወጥና ታላቅም በረዶ ሆነ።

## ሴቲቱና ዘንዶው

**12** ታላቅና አስደናቂ ምልክት በሰማይ ታየ፤ ፀሓይን የለበሰች፣ ጨረቃን ከእግሮቿ በታች የረገጠችና በራሷም ላይ ዐሥራ ሁለት ከዋክብት ያሉት አክሊል የደፋች አንዲት ሴት ታየች። [2]እርሷም ነፍሰ ጡር ነበረች፤ ልትወልድ ስትል ምጥ ይዞአት ተጨንቃ ጮኸች። [3]ከዚያም ሌላ ምልክት በሰማይ ታየ፤ እነሆ፤ ሰባት ራሶችና ዐሥር ቀንዶች የነበሩት፣ በራሶቹም ላይ ሰባት አክሊል የደፋ ታላቅ ቀይ ዘንዶ ታየ። [4]ጅራቱ የከዋክብትን አንድ ሦስተኛ ከሰማይ ስቦ ወደ ምድር ጣላቸው፤ እርሷም በወለደች ጊዜ ልጇን ለመዋጥ ፈልጎ ዘንዶው ልትወልድ በተቃረበችው ሴት ፊት ቆመ። [5]ሕዝቦችን ሁሉ በብረት በትር የሚገዛውን ወንድ ልጅ ወለደች፤ ልጇም ወደ እግዚአብሔርና ወደ ዙፋኑ ተነጠቀ። [6]ሴቲቱም አንድ ሺህ ሁለት መቶ ሥልሳ ቀን ክብካቤ እንዲ

አስ9፥19፡22፤ራእ3፥10
11፥11 ቍ9፤ ሕዝ37፥5፡9፡10፡14
11፥12 2ነገ2፥11፤ ሐሥ1፥9፤ራእ4፥1
11፥13 ራእ6፥12፤ 14፥7፤16፥9፡11፤19፥7
11፥14 ራእ8፥13
11፥15 መዝ145፥13፤ ዳን2፥44፤7፥14፡27፤ ሚክ4፥7፤ዘካ14፥9፤ ማቴ24፥31፤ሉቃ1፥33፤ ራእ12፥10፤16፥17፤ 19፥1
11፥16 ራእ4፥4፡10
11፥17 መዝ30፥12፤ ራእ1፥4፡8፤19፥6
11፥18 መዝ2፥1፤ ራእ10፥7፤19፥5፤ 20፥12
11፥19 ዘፀ25፥10-22፤ 2ዜና5፥7፤ዕብ9፥4፤ ራእ4፥5፤15፥5፡8፤ 16፥21
12፥1 ቍ3፤ዘፍ37፥9፤ ራእ11፥19
12፥2 ኢሳ26፥17፤ ገላ4፥19
12፥3 ቍ1፡9፡13፡ 16፡17፤ዳን7፥7፡20፤ ራእ13፥1፤15፥1፤17፥3፡7፡ 12፡16፤19፥15
12፥4 ዳን8፥10፤ ማቴ2፥16፤ራእ8፥7
12፥5 መዝ2፥9፤ ሐሥ8፥39፤ራእ2፥27፤ 19፥15
12፥6 ራእ11፥2

11፥11 *የሕይወት እስትንፋስ ከእግዚአብሔር ዘንድ መጥቶ ገባባቸው፤* እውነተኛ እምነት እንደ ነበራቸው ተመሰከረላቸው (ከሕዝ 37፥5፡10 ጋር ያነጻጽሩ)።

11፥12 *ጠላቶቻቸው እየተመለከቷቸው፤* ከ1፥7 ጋር ያነጻጽሩ። *በደመና ወደ ሰማይ ወጡ፤* ከ1ተሰ 4፥17 ጋር ያነጻጽሩ።

11፥13 *የምድር መናወጥ፤* የ6፥12 ማብ ይመ፤ እንዲሁም ሕዝ38፥19 ይመ። *ለሰማይም አምላክ ክብር ሰጡ፤* ክብር የሰጡት ንስሓ በመግባት ሳይሆን፣ የሁሉ እውነተኛ ጌታ ክርስቶስ እንጂ የክርስቶስ ተቃዋሚ አለመሆኑን በመገንዘብ ነው።

11፥14 *ሁለተኛው ወዮ፤* ከ9፥12 ጋር ያነጻጽሩ።

11፥15 *ሰባተኛውም መልአክ መለከቱን ነፋ፤* በተከታታይ መነፋት የጀመሩት መለከቶች በመቀጠል (9፥13 ይመ) ተፈጸሙ። *የጌታችን...መንግሥት፤* ከዘፀ15፥18፤ መዝ10፥16፤ ዘካ14፥9 ጋር ያነጻጽሩ። *የጌታችንና የእርሱ ክርስቶስ፤* ከመዝ2፥2 ጋር ያነጻጽሩ።

11፥16 *ሃያ አራቱ ሽማግሌዎች፤* የ4፥4 ማብ ይመ።

11፥17 *ያለህና የነበርህ፤* በ1፥4፡8፤4፥8 "የሚመጣው" ተብሎአል፤ ይህ አባባል እዚህ ላይ የተተወው መንግሥቱ አሁን እንደ ተጀመረ ተደርጎ ስለቀረበ ነው።

11፥18 *አሕዛብ ተቈጥተው ነበር፤* መዝ 48፥4 ይመ። *የአንተም ቍጣ፤* የ6፥16 ማብ ይመ። የእግዚአብሔር ቍጣ ድል ሲያደርግ በ14፥10-11፤ 16፥15-21፤ 20፥8-9 ላይ ይታያል። *በሙታን ላይ የምትፈርድበት፤* በ6፥10 ላይ የተነሣው ጥያቄ የመጨረሻውን መልስ ያገኘው በ20፥11-15 ላይ ነው። *ለአገልጋዮችህ ለነቢያት፤* ዳን 9፥6፡10፤ አሞ3፥7፤ዘካ 1፥6 ይመ።

11፥19 *የኪዳኑ ታቦት፤* የብሉይ ኪዳኑ ታቦት የተሠራው ከግራር እንጨት ነበር (ዘፀ10፥1-2)። ምልክት የነበረውም ዙፋኑን ወይም የእግዚአብሔርን በሕዝቡ መካከል መገኘት ነበር። የኪዳኑ ታቦት ደብዛው የጠፋው ናቡዘራዳን በኢየሩሳሌም የሚገኘውን ቤተ መቅደስ በደመሰሰበት ወቅት ሳይሆን አይቀርም (2ነገ 25፥8-10)። በአዲስ ኪዳን ታቦቱ የሚያመለክተው እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የገባውን ኪዳን በታማኝነት የሚጠብቅ መሆኑን ነው። *መብረቅ ... ታላቅም በረዶ፤* የ4፥5 ማብ ይመ።

12፥1 *ምልክት፤* ከዚህ በፊት ታይቶ የማይታወቅ ክሥተትንና ሁነትን የሚያመለክት ነው (ከሉቃ21፥11፡25፤ ሐሥ2፥19 ጋር ያነጻጽሩ)። *ፀሓይን የለበሰች ... አንዲት ሴት፤* በመሲሑ የሚያምነውን፣ "መሲሓዊ ኅብረተ ሰብ" የሚያመለክት ተምሳሌት (ትእምርት) ሊሆን ይችላል (ቍ 5 ይመ)። *ዐሥራ ሁለት ከዋክብት፤* ከዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል ነገዶች ጋር ያነጻጽሩ።

12፥2 *ተጨንቃ ጮኸች፤* ከዚህ ጋር ተመሳሳይ የሆነ አባባል ከሚገኝበትና የኢየሩሳሌምን ዳግም ልደት ከሚገልጸው ከኢሳ 66፥7 ጋር ያነጻጽሩ (ሚክ 4፥10 ይመ)።

12፥3 *ሰባት ራሶች፤* ሁለንታዊ የሆነ ጥበብ እንዳለው ያመለክታል (ከ13፥1 ጋር ያነጻጽሩ) *ዐሥር ቀንዶች፤* ብርቱ ኀይል እንዳለው ያሳያል። *ቀይ ዘንዶ፤* በቍ 9 ላይ ተመልክቷል (ከ20፥2 ጋር ያነጻጽሩ)። በጥንት ሕዝቦች ተረታ ተረት ውስጥ ዘንዶዎች ቍልፍ ቦታ አላቸው (በከነዓናውያን ተረታ ተረት ውስጥ ሌዋታን፣ በግብፃውያን ደግሞ ቀይ ዐዞ ሊጠቀሱ ይችላሉ)። እነዚህ ሁሉ በብሉይ ኪዳን ውስጥ የእግዚአብሔርንና የእስራኤልን ጠላቶች ለመግለጽ ተምሳሌታዊ በሆነ መንገድ ተጠቅሰዋል (መዝ 74፥14፤ ኢሳ27፥1፤ ሕዝ29፥3 ይመ)።

12፥5 *ወንድ ልጅ፤* መሲሑን ነው። *የብረት በትር፤* የ2፥27 ማብ ይመ። *ልጇ ወደ እግዚአብሔርና ... ተነጠቀ፤* ስለ የክርስቶስ ዕርገት ነው።

12፥6 *አንድ ሺህ ሁለት መቶ ሥልሳ ቀን፤* ለመንፈ

ደረግላት ስግዚስብሔር ወዳዘጋጀላት ስፍራ ወደ በረሓ ሸሸች::

[7]በሰማይም ጦርነት ሆነ፤ ሚካኤልና መላ እክቱ ከዘንዶው ጋር ተዋጉ፤ ዘንዶውና መላ እክቱም መልሰው ተዋጓቸው፤ [8]ነገር ግን ድል ተመቱ፤ በሰማይም የነበራቸውን ስፍራ ዐጡ:: [9]ታላቁ ዘንዶ፣ የጥንቱ እባብ ተጣለ፤ እርሱም ዲያብሎስ ወይም ሰይጣን ተብሎ የሚጠራው፣ ዓለምን ሁሉ የሚያስተው ነው፤ እርሱ ወደ ምድር ተጣለ፤ መላእክቱም ከእርሱ ጋር ተጣሉ::

[10]ከዚህ በኋላ ታላቅ ድምፅ በሰማይ እን ዲህ ሲል ሰማሁ፤

"አሁን የስምላካችን ማዳን፣ ኀይልና
 መንግሥት፣
 የእርሱ ክርስቶስ ሥልጣንም መጥቶአል::
ቀንና ሌሊት በስምላካችን ፊት ሲከሳቸው
 የነበረው፣
 የወንድሞቻችን ከሳሽ ተጥሎአልና::
[11]እነርሱም በበጉ ደም፣
 በምስክርነታቸውም ቃል፣
ድል ነሡት፤
 እስከ ሞት ድረስ እንኳ፣
 ለነፍሳቸው አልሳሱም::
[12]ስለዚህ ሰማያት ሆይ፣
 በውስጣቸውም የምትኖሩ ሆይ፣
ደስ ይበላችሁ፤
 ምድርና ባሕር ግን ወዮላችሁ!
ምክንያቱም ዲያብሎስ ጥቂት ዘመን ብቻ
 እንደ ቀረው ስላወቀ፣
 በታላቅ ቍጣ ተሞልቶ ወደ እናንተ
 ወርዶአል::

[13]ዘንዶው ወደ ምድር እንደ ተጣለ ባየ ጊዜ፣ ወንድ ልጅ የወለደችውን ሴት አሳደ ዳት:: [14]ሴቲቱም በበረሓ ወደ ተዘጋጀላት ስፍራ በርራ መሄድ እንድትችል ሁለት የታላቁ ንስር ክንፎች ተሰጣት፤ ይህም የሆ ነው በዚያ ከእባቡ ፊት ርቃ ለአንድ ዘመን፣ ለዘመናትና ለዘመን እኩሌታ በክብካቤ እን ድትኖር ነው:: [15]እባቡም ሴቲቱ በጐርፍ ተጠራርጋ እንድትወሰድ፣ እንደ ወንዝ ያለ ውሃ ከአፉ ተፋ:: [16]ምድር ግን ሴቲቱን ረዳቻት፤ አፏንም ከፍታ ዘንዶው ከአፉ ያፈሰሰውን ወንዝ ዋጠች:: [17]ዘንዶውም በሴ ቲቱ ላይ ተቈጣ፤ ከቀሩት ልጆቿም ጋር ሊዋጋ ሄደ፤ እነርሱ የስግዚስብሔርን ትእዛ ዛት የሚጠብቁና የኢየሱስን ምስክር አጥብ ቀው የያዙ ናቸው::

13 ዘንዶውም[ጎ1] በባሕሩ ዳር ቆሞ ነበር::

## ከባሕር የወጣው አውሬ

ከዚያም አንድ አውሬ ከባሕር ሲወጣ አየሁ፤ እርሱም ዐሥር ቀንዶችና ሰባት ራሶች ነበሩት፤ በቀንዶቹም ላይ ዐሥር ዘውዶች፣ በራሶቹም ላይ የስድብ ስሞች ነበሩት:: [2]ያየ ሁትም አውሬ ነብር ይመስል ነበር፤ ነገር ግን እግሮቹ የድብ፣ አፉ ደግሞ የአንበሳ አፍ ይመስል ነበር፤ ዘንዶው የራሱን ኀይ ልና የራሱን ዙፋን እንዲሁም ታላቅ ሥል ጣን ለአውሬው ሰጠው:: [3]ከአውሬው ራሶች አንዱ ለሞት የሚያደርስ ቍስል ያለበት ይመስል ነበር:: ነገር ግን ለሞት የሚያደር ሰው ቍስሉ ዳነ፤ ዓለም በሙሉ በመደነቅ አውሬውን ተከተለው:: [4]ሰዎችም ለዘንዶው ሰገዱለት፤ ምክንያቱም ሥልጣኑን ለአው ሬው ሰጥቶታል:: ደግሞም፣ "አውሬውን የሚመስል ማን ነው? ከእርሱስ ጋር ማን ሊዋጋ ይችላል?" በማለት ለአውሬው ሰገ ዱለት::

ጎ1 አንዳንድ የጥንት ቅጆች እኔም በባሕሩ ዳር ቆሜ ነበር ይላሉ::

12፥7 ቍ3፤ ማቴ25፥41፤ይሁ9
12፥9 ቍ15፤ ዘፍ3፥1-7፤ማቴ4፥10፤ 25፥41፤ሉቃ10፥18፤ ዮሐ12፥31፤ ራእ20፥2፡3፡8፡10
12፥10 ኢዮ1፥9-11፤ ዘካ3፥1፤1ጴጥ5፥8፤ ራእ77፥10፤11፥15
12፥11 ሉቃ14፥26፤ ዮሐ16፥33፤ራእ2፥10፤ 6፥9፤7፥14፤15፥2
12፥12 መዝ96፥11፤ ኢሳ44፥23፤49፥13፤ራ እ8፥13፤10፥6፤18፥20
12፥13 ቍ3፡5
12፥14 ዘፀ19፥4፤ ራእ11፥2
12፥15 ቍ9
12፥17 ዘፍ3፥15፤ ዮሐ14፥15፤ ራእ1፥2፤11፥7፤13፥7
13፥1 ዳን7፥1-6፤ 11፥36፤ራእ12፥3፤ 15፥2፤16፥13፤17፥3
13፥2 ዳን7፥4፡5፡6፤ ራእ2፥13፤16፥10
13፥3 ቍ12፡14፤ ራእ17፥8
13፥4 ዘፀ15፥11

ሳዊ ሕይወታችን የሚደረገው ጥበቃና በሕይወታችን ላይ የሚደር ሰው ስደት ተጓዳኝ ናቸው (የ11፥2 ማብ ይመ፤ ከ13፥5 ጋር ያነ ጻጽሩ):: *በረሓ፤* ምድረ በዳ ሳይሆን ለመንፈሳዊ ሕይወት የሚ ሆን ምሽግ ነው (ከሆሴ 2፥14 ጋር ያነጻጽሩ)::

12፥7 *ሚካኤል፤* በሰማይ በተደረገው ውጊያ ሰይጣንን ድል የነሣ ሊቀ መልአክ ነው:: በዳን12፥1 እንደጠቀሰው በመ ጨረሻው ዘመን ከሚሆነው መከራ እስራኤልን የሚታደግ የእስራ ኤል ጠባቂ ነው::

12፥9 *ዘንዶ ... ተጣለ፤* የመጀመሪያውን ሳይሆን የመጨረ ሻውን የሰይጣንን መጣል የሚገልጽ ነው፤ይህም ሰይጣን በመጨረ ሻው ዘመን የእግዚአብሔር ሕዝቦች ብርቱ ጠላት እንደሚሆን ያሳያል (ቍ12-17):: *ዲያብሎስ ወይም ሰይጣን፤* የ2፥9-10 ማብ ይመ:: *የሚያስተው፤* ከ2ቆሮ 11፥30 ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም ሉቃ 22፥31፤ ዮሐ13፥2 ይመ::

12፥10 *ከሳሽ፤* ኢዮ1፥9-11፤ ዘካ3፥1 ይመ:: በዕብራይስጥ ሰይጣን ማለት፣ "ከሳሽ" ማለት ነው::

12፥11 *በበጉ ደም፤* የ5፥9 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 1፥5፤ 7፥14 ይመ::

12፥12 *ጥቂት ዘመን ብቻ እንደቀረው፤* ሰይጣን በእግዚአ ብሔር ሕዝቦች ላይ በመጨረሻው ዘመን የሚያደርስባቸውን ብርቱ የመከራ ዘመን የሚገልጽ ነው::

*12፥13-16፤* በዘፀአት መጽሐፍ ላይ ካለው ተመሳሳይ ነገር ጋር ያነጻጽሩ::

12፥14 *በረሓ፤* የቍ 6 ማብ ይመ:: *ለአንድ ዘመን፣ ለዘ መናትና ለዘመን እኩሌታ፤* አንድ ዓመት ሲደመር ሁለት ዓመት ሲደመር ግማሽ ዓመት ነው (የ11፥2 ማብ ይመ)::

12፥16 *ምድር ... ረዳቻት፤ አፏንም ከፍታ፤* በዘኍ 16፥30-33 ላይ ምድር አፏን ከፍታ የቆሬን ሰዎች እንደዋጠች ተጽፎአል::

12፥17 *ከቀሩት ልጆቿም፤* በቍ5:13 ላይ የተጠቀሰውን ወንድ ልጅ እርሱም ክርስቶስን ሳይሆን በጥቅሉ አማኞችን ነው:: *የኢየሱስን ምስክር፤* ኢየሱስ የሰጠውን ምስክርነት ነው (ከ1፥2:9፤ ከ19፥10 ጋር ያነጻጽሩ)::

13፥1 *አውሬ ከባሕር ሲወጣ፤* በመጀመሪያ የተጠቀሰው በ11፥7 ላይ ነው:: አንዳንዶች አውሬው የሚያመለክተው የዚ ህን ዓለም ባለ ሥልጣኖች የምትወክለውን የሮምን ግዛተ አፄ ነው ይላሉ፤ ሌሎች ደግሞ ሥጋ ለብሶ የሚገለጠውን የክርስቶስን ተቃዋሚ ነው ይላሉ:: የዚህ ራእይ ዳራ ዳንኤል ስለ አራቱ ታላላቅ አራዊት የተናገረው ሊሆን ይችላል (ዳን 7፥2-7):: በ17፥8-11 ላይ ራእዩን የሚተረጕመው መልአክ ስለ አውሬው የሚናገረውን ይመ:: *ዐሥር ቀንዶች፤* 17፥12 ይመ:: *የስድብ ስሞች፤* የሮም ንጉሠ ነገሥቶች አማልክት በሚጠሩበት እነርሱም ይጠሩ ነበር:: ለምሳሌ ዶሚጥያኖስ፣ "ጌታችንና አምላካችን" ተብሎ ይጠራ ነበር::

13፥2 *ነብር ... የድብ ... የአንበሳ፤* ዮሐንስ በራእዩ ያያ ቸው አውሬዎች፣ ዳንኤል ስለ አራቱ አራዊት ባሕርያት የተናገ ረውን አጣምሮ የያዘ ነበር (ዳን 7፥4-6):: *ዘንዶው፤* የ12፥3 ማብ ይመ::

13፥3 *ለሞት የሚያደርሰው ቍስል ... ዳነ፤* አውሬው ታላቅ የማገገም ኀይል እንዳለው የሚያሳይ ነው:: *ዓለም በሙሉ በመደነቅ፤* የምድር ሕዝቦች ያሳዩትን ተመሳሳይ ባሕርይ በ17፥8 ላይ ይመ::

[5]አውሬው የትዕቢት ቃል የሚናገርበትና የሚሳደብበት አፍ ተሰጠው፤ አርባ ሁለት ወር በሥልጣን እንዲሠራም ተፈቀደለት። [6]እርሱም እግዚአብሔርን ለመሳደብ እንዲሁም ስሙንና ማደሪያውን፣ በሰማይም የሚኖሩትን ለመሳደብ አፉን ከፈተ። [7]ቅዱሳንን እንዲዋጋና ድልም እንዲነሣቸው ኀይል ተሰጠው። በነገድ፣ በወገን፣ በቋንቋና በሕዝብም ሁሉ ላይ ሥልጣን ተሰጠው። [8]ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ[*] በታረደው በግ የሕይወት መጽሐፍ ላይ ስሞቻቸው ያልተጻፈ የምድር ሰዎች ሁሉ ለአውሬው ይሰግዳሉ።

[9]ጆሮ ያለው ቢኖር ይስማ።

[10]ማንም የሚማረክ ቢኖር፣
  እርሱ ይማረካል፤
ማንም በሰይፍ የሚገድል[†] ቢኖር፣
  እርሱ በሰይፍ ይገደላል።

ይህም የቅዱሳን ትዕግሥትና እምነት የሚታየው በዚህ እንደ ሆነ ያስገነዝባል።

## ከምድር የወጣው አውሬ

[11]ከዚያም ሌላ አውሬ ከምድር ሲወጣ አየሁ፤ እርሱም እንደ በግ ሁለት ቀንዶች ነበሩት፤ ነገር ግን እንደ ዘንዶ ይናገር ነበር። [12]በመጀመሪያው አውሬ ስም በሙሉ ሥልጣን ይሠራ ነበር፤ ምድርና በእርሷም የሚኖሩ ሁሉ፣ ለሞት ከሚያደርሰው ቍስል የዳነውን የመጀመሪያውን አውሬ እንዲያመልኩ አደረገ። [13]በሰዎቹም ፊት እሳት ከሰማይ ወደ ምድር እስኪያወርድ ድረስ ታላላቅ ምልክቶችን አደረገ። [14]በመጀመሪያው አውሬ ስም ምልክቶችን እንዲያደርግ ሥልጣን ስለ ተሰጠው፣ በምድር የሚኖሩ ሰዎችን አሳተ፤ በሰይፍ ቈስሎ ለነበረው፣ ነገር ግን በሕይወት ለሚኖረው አውሬ ምስል እንዲያቆሙም አዘዛቸው። [15]ደግሞም የመጀመሪያው አውሬ ምስል መናገር እንዲችል ለምስሉ እስትንፋስ ለመስጠትና ለዚህም ምስል የማይሰግዱ ሁሉ እንዲገደሉ ለማድረግ ሥልጣን ተሰጠው። [16]እንዲሁም ታናናሾችና ታላላቆች፣ ሀብታሞችና ድኾች፣ ጌቶችና ባሮች ሁሉ በቀኝ እጃቸው ወይም በግምባራቸው ላይ ምልክት እንዲቀበሉ አስገደዳቸው፤ [17]ይህም የሆነው የአውሬው ምልክት፣ ይኸውም ስሙ ወይም የስሙ ቍጥር የሌለው ማንም ሰው ለመግዛትም ሆነ ለመሸጥ እንዳይችል ነው።

[18]ይህ ጥበብ ይጠይቃል፤ አእምሮ ያለው ማንኛውም ሰው የአውሬውን ቍጥር ያስላው፤ ምክንያቱም ቍጥሩ የሰው ቍጥር ነው። ቍጥሩ ስድስት መቶ ሥልሳ ስድስት ነው።

## በጉና መቶ አርባ አራቱ ሺህ ሰዎች

**14** ከዚህ በኋላ አየሁ፣ እነሆ፣ በጉ በጽዮን ተራራ ላይ ቆሞ ነበር፤ ከእርሱም ጋር የእርሱ ስምና የአባቱ ስም በግምባራቸው ላይ የተጻፈባቸው መቶ አርባ አራቱ ሺህ ሰዎች ነበሩ። [2]ከሰማይ እንደ ብዙ

13፥5 ዳን7፥8፡11፡20፡25፤11፥36፤2ተሰ2፥4፤ ራእ11፥21
13፥6 ራእ12፥12
13፥7 ዳን7፥21፤ ራእ5፥9፤7፥9፤10፥11፤ 11፥7፤17፥15
13፥8 ቍ12፡14፤ ማቴ25፥34፤ዮሐ1፥29፤ ራእ3፥10
13፥9 ራእ2፥7
13፥10 ኤር15፥2፤ 43፥11፤ዕብ6፥12፤ ራእ14፥12
13፥11 ቍ1፡2፤ ራእ16፥13
13፥12 ቍ3፡4፡14፡ 15፤ራእ14፥9፡11፤ 16፥2፤19፤20፤20፥4
13፥13 1ነገ18፥38፤ 2ነገ1፥10፤ማቴ24፥24፤ ሉቃ9፥54፤ራእ20፥9
13፥14 ቍ3፡12፤ 2ተሰ2፥9፡10፤ ራእ3፥10፤12፥9
13፥15 ቍ12፤ዳን3፥3-6
13፥16 ራእ7፥3፤14፥9፤ 19፥5፤20፥4
13፥17 ቍ18፤ ራእ14፥9፡11፤15፥2
13፥18 ራእ15፥2፤ 17፥9፤21፥17
14፥1 ቍ3፤መዝ2፥6፤ ዕብ12፥22፤ራእ3፥12፤ 5፥6፤7፥3፡4፤22፥4

[*]8 ወይም ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ስሞቻቸው በታረደው በግ የሕይወት መጽሐፍ ውስጥ የተጻፈው
[†]10 አንዳንድ የጥንት ቅጆች የሚገደል ይላሉ።

13፥5 *ተሰጠው፤* በግሪኩ ቅጂ ላይ ከቍ 5-7 ባለው ክፍል ብቻ "ተሰጠው" የሚለው ተገብሮ ግሥ አራት ጊዜ ተጠቅሶአል፤ ይህም አውሬው ከዘንዶው በታች መሆኑንና ለእርሱም የሚገዛ መሆኑን ያሳያል (ቍ 2፡4 ይመ)። *አርባ ሁለት ወር፤* የ11፥2 ማብ ይመ።

13፥7 *እንዲዋጋና፤* 12፥17፤ እንዲሁም ዳን 7፥7 ይመ።

13፥8 *በታረደው በግ የሕይወት መጽሐፍ፤* የ3፥5 ማብ ይመ። *ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ በታረደው፤* አማራጭ ትርጕሙን ይመ፤ ከ17፥8 እንዲሁም ከኢሳ53፥7፤ ዮሐ1፥29፡36 ጋር ያነጻጽሩ።

13፥11 *ሌላ አውሬ ከምድር ሲወጣ፤* አንዳንዶች ይህ ከምድር የሚወጣው አውሬ የሚያመለክተው የዚህን ዓለም ባለ ሥልጣኖችን የሚያገለግሉትን ሃይማኖታዊ ኀይሎችን ነው ይላሉ። ሌሎች ደግሞ ሥጋ ለብሶ የሚገለጠውን ሐሰተኛውን ነቢይ ነው ይላሉ (16፥13፤ 19፥20 እና 20፥10 ይመ)። *እንደ በግ ሁለት ቀንዶች ነበሩት፤* ትሑትና ቅን ለመምሰል መሞከሩን ያመለክታል። ኢየሱስ የበግ ለምድ ለብሰው ስለሚመጡ ጨካኝ ተኵላዎች በማቴ 7፥15 ውስጥ የሰጠውን ማስጠንቀቂያ ይመ።

13፥12 *በመጀመሪያው አውሬ ስም በሙሉ ሥልጣን ይሠራ ነበር፤* አሁን የክፉ ኀይሎች ሥላሴ ሙሉ ሆኖ እናገኘዋለን። ከምድር የወጣው አውሬ፣ ከባሕር በወጣው አውሬ ሥልጣን ሥር ነው፤ ከባሕር የወጣው አውሬ በዘንዶው ሥልጣን ሥር ነው። እነርሱም ሰይጣን፣ የዚህ ዓለም ሥልጣንና ሃይማኖታዊ ክሕደት (ወይም ሰይጣን፣ የክርስቶስ ተቃዋሚና ሐሰተኛው ነቢይ) ናቸው፤ እነዚህ በአንድነት የእግዚአብሔርን ሥራ ማለትም የአብን፣ የወልድንና የመንፈስ ቅዱስን ሥራ የሚቃወሙና የሚገዳደሩ ናቸው።

13፥13 *ምልክቶችን፤* በዘዳ13፥1-3 ላይ የተሰጠውን ማስጠንቀቂያ ይመ። እንደዚሁም ማቴ24፥24፤ 2ተሰ2፥9 ይመ። ከራእ 19፥20 ጋር ያነጻጽሩ። *እሳት ከሰማይ፤* 1ነገ 18፥24-39 ይመ።

13፥14 *ምስል እንዲያቆሙ፤* ከዳን 3፥1-11 እና ከ2ተሰ 2፥4 ጋር ያነጻጽሩ።

13፥15 *መናገር እንዲችል፤* በጥንት ሥነ ጽሑፎች ላይ ምስሎች ወይም ሐውልቶች ይናገራሉ የሚል እምነት በሰፊው ተጽፎ ይገኛል። በጥንቱ ዓለም ምስሎች ወይም ሐውልቶች እንደ ተናገሩ አድርጎ መናገርና ሌሎች ምትሃታዊ ሥራዎች የተለመዱ ናቸው።

13፥16 *ምልክት፤* ይህ የተወሰደው በባሪያዎች ወይም በጠላት ወታደሮች ላይ ከሚደረግ ምልክት ወይም በመንግሥት ሰነዶች ላይ ከሚደረግ ማኅተምና ቴምብር ወይም በአዲስ አማኞች ግምባር ላይ ከሚደረግ ምልክት ሊሆን ይችላል፤ የሆነ ሆኖ የአውሬው ምልክት የእርሱ አገልጋይ መሆንን ያመለክታል። የክርስቶስ ተቃዋሚ በሚነግሥበት በመጨረሻው ዘመን ይህ ትልቁ የታማኝነት መለኪያ ይሆናል (ከቍ17፤ 14፥9፡11፤ 15፥2፤ 16፥2፤ 19፥20፤ 20፥4 ጋር ያነጻጽሩ)። አውሬው ይህንን የሚያደርገው በም7 ላይ ስለ ታተሙት የእግዚአብሔር አገልጋዮች የተገለጸውን ለማስመሰል ነው።

13፥17 *ለመግዛትም ሆነ ለመሸጥ፤* ታማኝ አማኞች ሁሉ እንዳይሸጡና እንዳይገዙ የሚደረግ እገዳ ነው። *የስሙ ቍጥር፤* በጥንት ዘመን ፊደሎች እንደ ቍጥር ያገለግሉ ነበር። በዚያን ዘመን የሚነገሩ እንቆቅልሾች በስም ፈንታ እየገቡ እንደ ስም የሚያገለግሉ ቍጥሮችን ይጠቀሙ ነበር።

13፥18 *ስድስት መቶ ሥልሳ ስድስት፤* የእነዚህን ቍጥሮች ምስጢር ለመፍታት የተለያዩ ስልቶች የተሞከሩ ሲሆን፣ ቍጥሮች የሚወክሉት ሰዎችን ማለትም እንደ ኢውናተስ፣ ላቴኖስ ወይም ኔሮ ቄሣር የመሳሰሉትን ነው። ሌሎች ደግሞ ቍጥሩ የሚያመለክተው የክፉ ኀይሎችን ሥላሴ ነው ይላሉ፤ እያንዳንዱ አኀዝ ፍጹም ቍጥር ከሆነው ከ7 ቍጥር ስለሚያንስ፣ የክፉ ኀይሎች ሥላሴ እኩይ መሆኑን ያሳያል።

14፥1 *በጉ፤* የ5፥6 ማብ ይመ። *በጽዮን ተራራ፤* በብሉይ ኪዳን በመጀመሪያ የቅድመ እስራኤላውያን ምሽግ ስትሆን፣ ከዚያም በዳዊት ከተያዘች በኋላ ዋና ከተማው ሆናለች (2ሳሙ5፥7)። ከጊዜ በኋላ ደግሞ የኢየሩሳሌም ተለዋጭ ስም ሆነች። በዕብ 12፥22-24 እንደምናነበው ሁሉ፣ በራእየ ዮሐንስም ውስጥ ሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም የእግዚአብሔርና የሕዝቡ መኖሪያ ነች (ከገላ 4፥26 ጋር ያነጻጽሩ)፤ በ21፥2-3 ላይ እንደ ተጻፈው ወደ አዲሲቱ ምድር ትወርዳለች። *መቶ አርባ አራቱ ሺህ፤* የ7፥4 ማብ ይመ። *ስም፤* ከ13፥16-18 ጋር ያነጻጽሩ።

ውሃ ድምፅና እንደ ታላቅ ነጐድጓድ ድምፅ የመሰለ ድምፅ ሰማሁ፤ የሰማሁት ድምፅ በገና ደርዳሪዎች እንደሚደረድሩት ዐይነት ነበር። [3]እነርሱም በዙፋኑ ፊት፣ በአራቱ ሕያዋን ፍጡራንና በሽማግሌዎቹ ፊት አዲስ መዝሙር ዘመሩ። ከምድር ከተዋጁት ከመቶ አርባ አራቱ ሺህ ሰዎች በስተቀር መዝሙሩን ማንም ሊማረው አልቻለም። [4]እነዚህ ራሳቸውን በሴቶች ያላረከሱት ናቸው፤ ራሳቸውን በንጽሕና ጠብቀዋልና። በጉ ወደ ሚሄድበት ሁሉ ይከተሉታል፤ ለእግዚአብሔርና ለበጉ በኵራት እንዲሆኑ ከሰዎች መካከል የተዋጁ ናቸው። [5]በአፋቸው ምንም ዐይነት ውሸት አልተገኘም፤ ነቀፋም የለባቸውም።

### ሦስቱ መላእክት

[6]ከዚያም ሌላ መልአክ በሰማይ መካከል ሲበር አየሁ፤ እርሱም በምድር ላይ ለሚኖሩ ለሕዝብ፣ ለነገድ፣ ለቋንቋና ለወገን ሁሉ የሚሰብከውን የዘላለም ወንጌል ይዞ ነበር፤ [7]በታላቅ ድምፅም፣ "እግዚአብሔርን ፍሩ፤ ክብርም ስጡት፤ ምክንያቱም የፍርዱ ሰዓት ደርሶአል፤ ሰማይንና ምድርን፣ ባሕርንና የውሃ ምንጮችን ለፈጠረው ስገዱ" አለ።

[8]ሌላም ሁለተኛ መልአክ፣ "ሕዝቦች ሁሉ የዝሙቷን ቍጣ ወይን ጠጅ እንዲጠጡ ያደረገች ታላቂቱ ባቢሎን ወደቀች! ወደቀች!" እያለ ተከተለው።

[9]ሦስተኛውም መልአክ በታላቅ ድምፅ እንዲህ እያለ ተከተላቸው፤ "ማንም ለአውሬው ና ለምስሉ የሚሰግድ፣ ምልክቱንም በግምባሩ ወይም በእጁ ላይ የሚቀበል ቢኖር፣ [10]እርሱ ደግሞ ምንም ነገር ሳይቀላቀልበት በቍጣው ጽዋ ውስጥ የተቀየጠውን የእግዚአብሔርን ቍጣ ወይን ጠጅ ይጠጣል። በቅዱሳን መላእክትና በበጉ ፊትም በእሳትና በዲን ይሠቃያል። [11]የሥቃያቸውም ጢስ ከዘላለም እስከ ዘላለም ወደ ላይ ይወጣል። ለአውሬው ና ለምስሉ የሚሰግዱ ወይም የስሙንም ምልክት የሚቀበሉ ሁሉ ቀንና ሌሊት ዕረፍት የላቸውም።" [12]የእግዚአብሔርን ትእዛዛት የሚጠብቁና ለኢየሱስም ታማኝ ሆነው በትዕግሥት የሚጸኑ ቅዱሳን የሚታወቁት በዚህ ነው።

[13]ከዚያም፣ "ከእንግዲህ ወዲህ በጌታ ሆነው የሚሞቱ ብፁዓን ናቸው ብለህ ጻፍ" የሚል ድምፅ ከሰማይ ሰማሁ።

መንፈስም፣ "አዎ፣ ሥራቸው ስለሚከተላቸው ከድካማቸው ያርፋሉ" ይላል።

### የምድር መከር ጊዜ

[14]አየሁም፤ እነሆ፤ በፊቴ ነጭ ደመና ነበረ፤ በደመናውም ላይ፣ "የሰውን ልጅ የሚመስል" ተቀምጦ ነበር፤ እርሱም በራሱ ላይ የወርቅ አክሊል ደፍቶ፣ በእጁም ስለታም ማጭድ ይዞ ነበር። [15]ሌላም መልአክ ከመቅደሱ ወጥቶ በደመናው ላይ ለተቀመጠው፣ "የዐጨዳው ሰዓት ስለ ደረሰ፣ ማጭድህን ይዘህ ዕጨድ፤ የምድር መከር ደርሶአልና" ሲል በታላቅ ድምፅ ጮኸ። [16]ስለዚህ በደመናው ላይ የተቀመጠው ማጭዱን ወደ ምድር ሰደደ፤ ምድርም ታጨደች።

[17]ሌላም መልአክ በሰማይ ካለው መቅደስ ወጣ፤ እርሱም እንዲሁ ስለታም ማጭድ ነበረው፤ [18]በእሳት ላይ ሥልጣን ያለው ሌላ መልአክ ከመሠዊያው ወጥቶ ስለታም

14፥2 ራእ1፥15፤ 5፥8፤6፥1፥15፥2
14፥3 ቍ1፤ራእ4፥4፡ 6፤5፥9
14፥4 2ቆሮ11፥2፤ያዕ1፥18፤ ራእ3፥4፤5፥9፤7፥17
14፥5 መዝ32፥2፤ ሶፎ3፥13፤የሐ1፥47፤ ኤፌ5፥27፤1ጴጥ2፥22
14፥6 ራእ3፥10፤ 8፥13፤13፥7፤19፥17
14፥7 መዝ34፥9፤ ራእ8፥10፤6፥11፥13፤ 15፥4፤16፥4
14፥8 ኢሳ21፥9፤ ኤር51፥8፤ራእ16፥19፤ 17፥2፥4፤5፤18፥2፥3፥9፥10
14፥9 ራእ13፥12፡ 14፡16
14፥10 ኢሳ51፥17፤ ኤር25፥15፤51፥7፤ ራእ9፥17፤18፥6
14፥11 ቍ9፤ኢሳ34፥10፤ ራእ4፥8፤13፥12፡ 17፤19፥3
14፥12 ዮሐ14፥15፤ ዕብ6፥12፤ራእ13፥10
14፥13 1ቆሮ15፥18፤ 1ተሰ4፥16፤ራእ2፥7፤ 22፥17
14፥14 ዳን7፥13፤ ማቴ17፥5፤ራእ1፥13፤ 6፥2
14፥15 ቍ17፡18፤ ኤር51፥33፤ኢዩ3፥13፤ ማር4፥29፤ራእ11፥19
14፥17 ቍ15
14፥18 ቍ15፤ ራእ6፥9፤ 8፥5፤16፥7

14፥2 *በገና፤* የ5፥8 ማብ ይመ።

14፥3 *አዲስ መዝሙር፤* የ5፥9 ማብ ይመ። የመዝሙሩ ጭብጥ ስለ እግዚአብሔር ማዳን የሚያወሳ ነው።

14፥4 *ራሳቸውን በሴቶች ያላረከሱት፤* ይህ ተምሳሌት የሚያመለክተው ራሳቸውን ከአረማዊው ዓለም ሥርዐት የጠበቁ አማኞችን ሊሆን ይችላል። *በጉ ... ይከተሉታል፤* ደቀ መዛሙርቱ እንደ ተከተሉት ማለት ነው (ማቴ19፥21፤ ማር8፥34 ይመ)። *በኵራት፤* ዘሌ23፥9-14 ይመ። በአዲስ ኪዳን ውስጥ ይህ ቃል የገባው በአንድ የተወሰነ ክልል ወደ ጌታ የመጡትን የመጀመሪያ ሰዎች (ሮሜ 16፥5) ወይም ከሙታን በመነሣት የመጀመሪያ የሆኑትን ሰዎች (1ቆሮ15፥20) ለማመልከት ነው። በራእየ ዮሐንስ ውስጥ አማኞች ለእግዚአብሔርና ለበጉ የሚቀርቡ ምርጥ መሥዋዕት ናቸው።

14፥5 *በአፋቸው ... ውሸት አልተገኘም፤* ከሮሜ 1፥25 ጋር ያነጻጽሩ፤ ኢሳ 53፥9 ይመ።

14፥6 *የዘላለም ወንጌል፤* የዚህ፣ "መልካም ዜና" ይዘት ምናልባት በቍ 7 ላይ የሚገኘው ሊሆን ይችላል።

14፥7 *ሰማይን ... ለፈጠረው፤* ዘፀ20፥11፤ መዝ146፥6 ይመ።

14፥8 *የዝሙቷን ... ወይን ጠጅ፤* እዚህ ላይ የቀረቡት እንደ አመንዝራ ሲሆን፣ የረከሰ ተግባራቸውን የሚያከናውኑት በመስከር ነው። *ታላቂቱ ባቢሎን፤* በመስጴጦምያ የምትገኘው የጥንቷ ባቢሎን በፖለቲካ፣ በንግድና በሃይማኖት ረገድ የዓለም መንግሥታት ማእከል ነበረች። ባቢሎን በምቾትና በምግባረ ብልሹነት የታወቀች ናት። "ታላቂቱ ባቢሎን" የሚለው ስያሜ የተወሰደው ከዳን 4፥30 ላይ ነው። አንዳንድ ሊቃውንት እንደሚናገሩት፣ ይህ ስያሜ በራእየ ዮሐንስ ውስጥ የገባው የእግዚአብሔርና የሕዝቡ ጠላት የሆነውን ዓለም ወክላ የምትቀመጠውን ሮምን ለመግለጽ ነው (ለምሳሌ እዚህ ላይ እና በ16፥19፤ 17፥5፤ 18፥2፥10፥21 ላይ ያለውን ይመ)። ሌሎች ደግሞ በጥቅሉ የዓለምን ፖለቲካዊና ሃይማኖታዊ ሥርዐት ለመወከል ነው ይላሉ። ሌሎች ግን እንደ ገና የምትሠራዋንና የምትታደሰዋን ባቢሎንን ለመግለጽ ነው ይላሉ። የባቢሎን መውደቅ በኢሳ21፥9፤ በኤር 51፥8 ላይ ተነግሮአል።

14፥10 *በቍጣው ጽዋ፤* በብሉይ ኪዳን የእግዚአብሔር ቍጣ ብዙ ጊዜ የተመሰለው ሊጠጣ በጽዋ እንደቀረበ የወይን ጠጅ ነው (መዝ75፥8፤ ኢሳ51፥17፤ ኤር25፥15)። የእግዚአብሔር ቍጣ የበቀል ቅጣት ሳይሆን፣ ፍቅሩንና ጸጋውን ባልተቀበሉ ሁሉ ላይ የሚመጣ የጻድቅ እግዚአብሔር ቅጣት ነው። *በእሳትና በዲን፤* ሰዶምና ገሞራ የጠፉት በእሳትና በዲን ነው (ዘፍ 19፥24)። ክፉዎች ተመሳሳይ ዕጣ እንደሚጠብቃቸው በመዝ11፥6 ላይ ተነግሮአል። ይህ አገላለጽ በብሉይ ኪዳንና በአዋልድ መጻሕፍት ውስጥ ይገኛል። ይህ ሐረግ በራእየ ዮሐንስ የመጨረሻዎቹ ምዕራፎች ውስጥ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶአል (19፥20፤ 20፥10፤ 21፥8)።

14፥11 *የሥቃያቸውም ጢስ ከዘላለም እስከ ዘላለም፤* 19፥20 ከ20፥10 ጋር ያነጻጽሩ።

14፥13 *ብፁዓን፤* ለሁለተኛ ጊዜ የተጠቀሰ ቃል ነው (የ1፥3 ማብ ይመ)።

14፥14 *የሰውን ልጅ፤* 1፥13 እንዲሁም የዳን7፥13፤ ማር 8፥31 ማብ ይመ። *የወርቅ አክሊል፤* ድል ለነሣ የሚሰጥ ወርቅ ነው። በድል አክሊልና በንጉሣዊ አክሊል መካከል ያለውን ንጽጽር ለማየት የ2፥10 ማብ ይመ። *ማጭድ፤* እስራኤላውያን ሰብል ለማጨድ የሚጠቀሙበት ማጭድ የሚሠራው ከባልጩት ወይም ከብረት ሲሆን፣ እጀታው ደግሞ ከዕንጨት ወይም ከቀንድ ነው።

14፥15 *የምድር መከር፤* በጥቅሉ የሚያመለክተው ወደ ፊት የሚመጣውን ፍርድ ነው (ማቴ13፥30፤ 40-42 ይመ)። አንዳንድ ሊቃውንት ይህ ሐረግ የሚያወሳው ክርስቶስ ዳግም ተመልሶ በሚመጣበት ጊዜ ስለሚሆነው የጻድቃን መሰብሰብ ነው ይላሉ።

14፥18 *በእሳት ላይ ሥልጣን ያለው ሌላ መልአክ፤*

ማጭድ የያዘውን፣ "ዘለላው ስለ በሰለ፣ ስለታም ማጭድህን ያዝና በምድር ላይ ያሉትን የወይን ዘለላዎች ሰብስብ" ሲል በታላቅ ድምፅ ጮኸ:: [19]መልአኩም ማጭዱን ወደ ምድር ሰደደ፤ የምድርን የወይን ዘለላዎች ሰብስቦ ወደ ታላቁ ወደ እግዚአብሔር የቍጣ ወይን መጭመቂያ ጣላቸው:: [20]ወይኑም ከከተማው ውጭ በወይን መጭመቂያ ውስጥ ተረገጠ፤ ከፍታው እስከ ፈረስ ልጓም የሚደርስ፣ ርዝመቱ ሦስት መቶ ኪሎ ሜትር ያህል ደም ከመጭመቂያው ወጣ::

## ሰባቱ መላእክትና ሰባቱ መቅሠፍቶች

**15** ሌላም ታላቅና አስደናቂ ምልክት በሰማይ አየሁ፤ የመጨረሻዎቹን ሰባት መቅሠፍቶች የያዙ ሰባት መላእክት አየሁ፤ የመጨረሻ የተባሉትም የእግዚአብሔር ቍጣ የሚፈጸመው በእርሱ በመሆኑ ነው:: [2]ከእሳት ጋር የተቀላቀለ የብርጭቆ ባሕር የሚመስል አየሁ፤ በባሕሩም አጠገብ አውሬውን፣ ምስሉንና የስሙን ቍጥር ድል የነሡትን ቆመው አየሁ፤ እነርሱም ከእግዚአብሔር የተሰጣቸውን በገና ይዘው፣ [3]የእግዚአብሔር ባሪያ የሆነውን የሙሴን መዝሙርና የበጉን መዝሙር እንዲህ እያሉ ይዘምሩ ነበር፤

"ሁሉን ቻይ ጌታ አምላክ ሆይ፤
ሥራህ ታላቅና አስደናቂ ነው::
የዘመናት[ሀ] ንጉሥ ሆይ፤
መንገድህ ጽድቅና እውነት ነው::
[4]ጌታ ሆይ፤ አንተን የማይፈራ፣
ስምህን የማያከብርስ ማን ነው?
አንተ ብቻ ቅዱስ ነህና::
የጽድቅ ሥራህ ስለ ተገለጠ፣
ሕዝቦች ሁሉ ይመጣሉ፤
በፊትህም ይሰግዳሉ::

[5]ከዚህ በኋላም አየሁ፤ በሰማይ ያለው ቤተ መቅደስ፣ ይኸውም የምስክሩ ድንኳን ተከፍቶ ነበር፤ [6]ሰባቱን መቅሠፍቶች የያዙት ሰባቱ መላእክት ከቤተ መቅደሱ ወጡ፤ እነርሱም ከተልባ እግር የተሠራ ንጹሕ የሚያበራ ልብስ ለብሰው፣ ደረታቸውንም በወርቅ መታጠቂያ ታጥቀው ነበር:: [7]ከዚያም ከአራቱ ሕያዋን ፍጡራን አንዱ ከዘላለም እስከ ዘላለም በሚኖረው አምላክ ቍጣ የተሞሉትን ሰባት የወርቅ ጽዋዎች ለሰባቱ መላእክት ሰጣቸው:: [8]ቤተ መቅደሱም ከእግዚአብሔር ክብር፣ ከኀይሉም በወጣው ጢስ ተሞላ፤ የሰባቱ መላእክት ሰባት መቅሠፍቶች እስኪፈጸሙ ድረስ ማንም ወደ ቤተ መቅደሱ መግባት አልቻለም::

## ሰባቱ የእግዚአብሔር ቍጣ ጽዋዎች

**16** ከዚያም ለሰባቱ መላእክት፣ "ሂዱ፤ ሰባቱን የእግዚአብሔር ቍጣ ጽዋዎች በምድር ላይ አፍስሱ" የሚል ታላቅ ድምፅ ከቤተ መቅደሱ ሰማሁ::

[2]የመጀመሪያው መልአክ ሄዶ ጽዋውን በምድር ላይ አፈሰሰ፤ የአውሬውን ምልክት በተቀበሉትና ለምስሉም በሰገዱት ሰዎች ላይ ክፉኛ የሚያሠቃይ ቍስል ወጣባቸው::

[3]ሁለተኛው መልአክ ጽዋውን በባሕር ላይ አፈሰሰ፤ ባሕሩም እንደ ሞተ ሰው ደም ሆነ፤ በባሕሩ ውስጥ የሚኖሩ ሕይወት ያላቸው ነገሮች ሁሉ ሞቱ::

[4]ሦስተኛው መልአክ ጽዋውን በወንዞችና በውሃ ምንጮች ላይ አፈሰሰ፤ እነርሱም

[ሀ]3 አንዳንድ የጥንት ቅጆች ሕዝቦች ይላሉ::

14፥19 ራእ19፥15
14፥20 ቍ19፤ ዘፍ49፥11፤ ዘዳ32፥14፤ ኢሳ63፥3፤ ኢዩ3፥13፤ ዕብ13፥12፤ ራእ11፥8፤ 19፥15
15፥1 ቍ6-8፤ ዘሌ26፥21፤ ራእ9፥20፤ 12፥1:3፤
15፥2 ራእ4፥6፤ 5፥8፤ 12፥11፤ 13፥1:14:17፤ 14፥2
15፥3 ዘፀ15፥1፤ ኢያ1፥1፤ መዝ112፥2፤ 145፥17፤ ራእ1፥8፤ 5፥9
15፥4 መዝ86፥9፤ ኢሳ66፥23፤ ኤር10፥7፤ ራእ19፥8
15፥5 ዘፀ38፥21፤ ዘኍ1፥50፤ ማቴ3፥16፤ ራእ11፥19
15፥6 ቍ1፤ ሕዝ9፥2፤ ዳን10፥5፤ ራእ1፥13፤ 14፥15
15፥7 ቍ1፤ ራእ1፥18፤ 4፥6
15፥8 ዘፀ40፥34:35፤ 1ነገ8፥10:11፤ 2ዜና5፥13:14፤ ኢሳ6፥4
16፥1 ቍ2-21፤ መዝ79፥6፤ ሶፎ3፥8፤ ራእ11፥19፤ 15፥1
16፥2 ቍ11፤ ዘፀ9፥9-11፤ ዘዳ28፥35፤ ራእ8፥7፤ 13፥15-17፤ 14፥9
16፥3 ዘፀ7፥17-21፤ ራእ8፥8:9፤ 11፥6
16፥4 ዘፀ7፥17-21፤ ራእ8፥10

በ8፥3-5 ላይ የተጠቀሰው መልአክ ነው:: እሳት አብዛኛውን ጊዜ የሚያያዘው ከፍርድ ጋር ነው (ማቴ18፥8፤ ሉቃ9፥54፤ 2ተሰ1፥7 ይመ) *ስለታም ማጭድ፤* ከዐውዱ እንደምንረዳው ይህ ማጭድ በቍ14 ላይ ከተጠቀሰው ማጭድ ይለያል:: ገበሬው የወይን ዘለላዎችን የሚቈርጥበት ትንሽ ቢላዋ ነው::

14፥19 *ወይን መጭመቂያ፤* ከተወቀረ ዐለት የሚሠራ ገንዳ ሲሆን ጠቅላላ ስፋቱ 6 ካሬ ሜትር ይሆናል፤ ይህ ከላይ በኩል የሚሠራው ገንዳ ነው፤ ከታች በኩል ሌላ አነስተኛ ገንዳ ተሠርቶ ሁለቱ ገንዳዎች በቦይ እንዲገናኙ ይደረጋል:: ከላይ በኩል በሚገኘው ገንዳ ውስጥ የወይኑ ዘለላ ከተጨመረ በኋላ በባዶ እግር ይረገጣል:: ጭማቂው በቦዩ እየወረደ ከታች በኩል ባለው ገንዳ ውስጥ ይጠራቀማል:: በብሉይ ኪዳን የወይን መረገጥ የሚያሳየው የመለኮትን ቍጣ ነው (ኢሳ63፥3፤ ሰቆ1፥15፤ ኢዩ3፥13 ይመ)::

14፥20 *ከከተማው ውጭ፤* ደም መፋሰስ ከተማውን ያረክሳል (ኢዩ3፥12-14፤ ዘካ14፥1-4፤ ይመ፤ ከዕብ13፥12 ጋር ያነጻጽሩ):: *ሦስት መቶ ኪሎ ሜትር፤* በግምት ከሰሜን እስከ ደቡብ ያለውን የፓሌስቲና ስፋት ያክላል::

*15፥1-8፤* ከሦስቱ ተከታታይ መቅሠፍቶች የመጨረሻ የሆኑትን ሰባቱን የቍጣ ጽዋዎች ባጭሩ የሚናገር ክፍል ነው:: (የ8፥2 ማብ ይመ)::

15፥1 *የእግዚአብሔር ቍጣ፤* የ6፥16 ማብ ይመ::

15፥2 *የብርጭቆ ባሕር፤* የ4፥6 ማብ ይመ:: *አውሬውን... ድል የነሡትን፤* በ12፥11 ላይ ዲያብሎስን ድል ከነሡት ቅዱሳን ጋር ያነጻጽሩ:: *የስሙን ቍጥር፤* የ13፥16-18 ማብ ይመ:: *በገና፤* የ5፥8 ማብ ይመ::

15፥3 *የሙሴን መዝሙርና፤* ዘፀ15፤ ዘዳ32 ይመ:: ዘፀ 15፥1-8 እስራኤላውያን ከግብፅ ባርነት ነጻ የወጡበትን ታላቅ ድል ለማክበር በሰንበት ምሽት በምኵራብ ይዘመር ነበር:: *የበጉን መዝሙር፤* ከሙታን የተነሣው ጌታ ለተከታዮቹ መንፈሳዊ ነጻነት በማስገኘት በጠላቶቹ ላይ ድል ተቀዳጅቷል (ከመዝ 22 ጋር ያነጻጽሩ):: *ሁሉን ቻይ፤* የ1፥8 ማብ ይመ:: *ሥራህ ታላቅና አስደናቂ ነው፤* ዘፀ15፥11፤ መዝ92፥5፤ 111፥2 ይመ:: *የዘመናት ንጉሥ፤* ኤር10፥10 ይመ፤ ከ1ጢሞ1፥17 ጋር ያነጻጽሩ::

*15፥4፤* መላው ፍጥረት ለእግዚአብሔር ክብር እንደሚሰጥ ብሉይና (መዝ 86፥9፤ ኢሳ 45፥22-23፤ ሚል1፥11) አዲስ ኪዳን (ፊል 2፥9-11) አስተምረዋል::

15፥5 *የምስክሩ ድንኳን፤* እስራኤላውያን በምድረ በዳ ይንከራተቱ በነበረበት ወቅት የእግዚአብሔር ማደሪያ ነበር (ዘፀ 40፥34-35 ይመ):: ስሙ የተሰጠው፣ ከሲና ተራራ የወረዱት ሁለቱ የምስክር ጽላቶች የሚገኙት በጥንቱ ድንኳን ውስጥ በመሆኑ ነው (ዘፀ32፥15፤ 38፥21፤ ዘዳ10፥5)::

15፥6 *ሰባቱን መቅሠፍቶች፤* ከተከታታዮቹ መቅሠፍ ቶች የመጨረሻው ነው (ቍ1 ይመ):: *በወርቅ መታጠቂያ፤* የንጉሥነትና የክህነት አገልግሎት ምሳሌ ነው::

15፥7 *አምላክ ቍጣ፤* ከ2ተሰ 1፥7-9 ጋር ያነጻጽሩ::

15፥8 *ጢስ ተሞላ፤* ከዘፀ40፥34፤ 1ነገ8፥10-11፤ ሕዝ44፥4 ጋር ያነጻጽሩ:: ጢስ የእግዚአብሔር ኀይልና ክብር ምሳሌ ነው::

16፥2 *በምድር፤* የመጀመሪያዎቹን አራት ጽዋዎች (ቍ2-9) ከመጀመሪያዎቹ አራት መለከቶች ጋር ያነጻጽሩ (8፥7-12):: *የአውሬውን ምልክት፤* የ13፥16 እና ማብ ይመ:: *ክፉኛ የሚያሠቃይ ቍስል፤* ስድስተኛው መቅሠፍት በግብፃውያን ላይ ያስከተለውን ብርቱ ቍስል ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ (ዘፀ9፥9-11፤ እንዲሁም ኢዮ2፥7-8:13)::

16፥4 *በወንዞችና በውሃ ምንጮች፤* ከ8፥10-11 ጋር ያነጻጽሩ፤ እንዲሁም መዝ 78፥44 ይመ::

ደም ሆኑ:: 5ከዚያም በውሆች ላይ ሥልጣን ያለው መልአክ እንዲህ ሲል ሰማሁ፤

“ያለህና የነበርህ ቅዱሱ ሆይ፤
 እንዲህ ስለ ፈረድህ፣
 አንተ ጻድቅ ነህ፤
6የቅዱሳንንና የነቢያትን ደም ስላፈሰሱ፣
 አንተም ደግሞ ደም እንዲጠጡ
  አደረግሃቸው፤ ይህ የሚገባቸው ነውና::”

7እንዲሁም ከመሠዊያው እንዲህ የሚል ድምፅ ሰማሁ፤

“አዎን፤ ሁሉን ቻይ ጌታ አምላክ ሆይ፤
 ፍርድህ እውነትና ጽድቅ ነው”

8አራተኛውም መልአክ ጽዋውን በፀሐይ ላይ አፈሰሰ፤ ፀሐይም ሰዎችን በእሳት እንድታቃጥል ኀይል ተሰጣት:: 9እነርሱም በታላቅ ሐሩር ተቃጠሉ፤ በእነዚህም መቅሠፍቶች ላይ ሥልጣን ያለውን የእግዚአብሔርን ስም ተሳደቡ እንጂ ንስሓ አልገቡም፤ ክብርም አልሰጡትም::

10አምስተኛውም መልአክ ጽዋውን በአውሬው ዙፋን ላይ አፈሰሰ፤ የአውሬውም መንግሥት በጨለማ ተዋጠ፤ ሰዎችም ከሥቃያቸው የተነሣ ምላሳቸውን ያኝኩ ነበር፤ 11ደግሞም ከሥቃያቸውና ከቍስላቸው የተነሣ የሰማይን አምላክ ተሳደቡ እንጂ ከሥራቸው ንስሓ አልገቡም::

12ስድስተኛውም መልአክ ጽዋውን በታላቁ ወንዝ በኤፍራጥስ ላይ አፈሰሰ፤ ከምሥራቅ ለሚመጡ ነገሥታት መንገድ እንዲዘጋጅላቸው የወንዙ ውሃ ደረቀ:: 13ከዚያም ከዘንዶው አፍ፣ ከአውሬው አፍና ከሐሰተኛው ነቢይ አፍ እንቍራሪት የሚመስሉ ሦስት ርኩሳን መናፍስት ሲወጡ አየሁ:: 14እነርሱም ምልክቶች የሚያደርጉ የአጋንንት መናፍስት ናቸው፤ ሁሉን በሚችል አምላክ ታላቅ ቀን ለሚሆነው ጦርነት እንዲሰበስቧቸው ወደ ዓለም ሁሉ ነገሥታት ይሄዳሉ::

15“እነሆ፤ እንደ ሌባ እመጣለሁ፤ ዕራቍቱን እንዳይሆን ኀፍረቱም እንዳይታይ ነቅቶ ልብሱን የሚጠብቅ ሰው ብፁዕ ነው::”

16እነርሱም ነገሥታቱን በዕብራይስጥ አርማጌዶን በሚባል ስፍራ ሰበሰቧቸው::

17ሰባተኛውም መልአክ ጽዋውን በአየር ላይ አፈሰሰ፤ በቤተ መቅደሱ ውስጥ ካለው ዙፋን “ተፈጸመ” የሚል ታላቅ ድምፅ ወጣ:: 18ከዚያም መብረቅ፣ ድምፅ፣ ነጐድጓድና ታላቅ የምድር መናወጥ ሆነ፤ ሰው በምድር ላይ ከተፈጠረ ጀምሮ እንዲህ ያለ ታላቅ የምድር መናወጥ ታይቶ አይታወቅም፤ ነውጡም እጅግ ታላቅ ነበር:: 19ታላቂቱ ከተማ ከሦስት ተከፈለች፤ የሕዝቦች ከተሞችም ፈራረሱ፤ እግዚአብሔርም ታላቂቱን ባቢሎን አስታወሰ፤ በብርቱ ቍጣው ወይን ጠጅ የተሞላውን ጽዋ ሰጣት:: 20ደሴቶች ሁሉ ሸሹ፤ ተራሮችም ሊገኙ አልቻሉም:: 21በሚዛን ሲመዘን እያንዳንዱ አርባ አምስት ኪሎ ግራም የሚሆን ታላቅ በረዶ በሰዎች ላይ ከሰማይ ወረደባቸው፤ መቅሠፍቱ እጅግ አሠቃቂ ስለ ነበር፣ ሰዎቹ ከበረዶው መቅሠፍት የተነሣ እግዚአብሔርን ተሳደቡ::

## በአውሬው ላይ የተቀመጠችው ሴት

**17** ሰባቱን ጽዋዎች ከያዙት ከሰባቱ መላእክት አንዱ መጥቶ እንዲህ አለኝ፤ “ና፤ በብዙ ውሆች ላይ የተቀመጠችውን የታላቂቱን አመንዝራ ፍርድ አሳይሃለሁ:: 2የምድር ነገሥታት ከእርሷ ጋር አመንዝረሩ፤ የምድር ነዋሪዎችም በዝሙቷ የወይን ጠጅ ሰከሩ::”

3ቀጥሎም መልአኩ በመንፈስ ወደ በረሓ ወሰደኝ፤ በዚያም አንዲት ሴት በስድብ ስሞች በተሞላ፣ ሰባት ራሶችና ዐሥር ቀን

16፥5 ራእ1፥4፤6፥10፤ 15፥3፡4
16፥6 ኢሳ49፥26፤ ሉቃ11፥49-51፤ ራእ1፥8፤6፥9፤14፥18፤ 15፥3፤19፥2
16፥8 ራእ6፥12፤ 8፥12፤14፥18
16፥9 ቍ11፡21፤ ራእ2፥21፤11፥13
16፥10 ዘፀ10፥21-23፤ ኢሳ8፥22፤ራእ8፥12፤ 9፥2፤13፥2
16፥11 ቍ2፡9፡21፤ ራእ2፥21፤11፥13
16፥12 ኢሳ11፥15፡ 16፤41፥2፤46፥11፤ ራእ9፥14
16፥13 ዘፀ8፥6፤ራእ 12፥3፤13፥1፤ 8፥2፤19፥20፤20፥10
16፥14 ማቴ24፥14፡24፤ 1ጢሞ4፥1፤ 6፥17፤17፥14፤19፥19፤ 20፥8
16፥15 ሉቃ12፥37፡ 39፤ራእ3፥18
16፥16 ቍ14፤መሳ 5፥19፤2ነገ23፥29፡29፡ 30፤ዘካ12፥11፤ራእ 9፥11
16፥17 ኤፌ2፥2፤ ራእ11፥15፤14፥15፤21፥6
16፥18 ዳን12፥1፤ ማቴ24፥21፤ ራእ4፥5፤6፥12
16፥19 ራእ14፥8፡ 10፤17፥18፤18፥5
16፥20 ራእ6፥14
16፥21 ቍ9፡11፤ ዘፀ9፥23-25፤ሕዝ 13፥13፤ 38፥22፤ ራእ8፥7፤11፥19
17፥1 ቍ5፡15፡16፤ ኢሳ23፥17፤ ኤር51፥13፤ራእ15፥1፡ 7፤16፥19፤ራእ19፥2
17፥2 ራእ14፥8
17፥3 ራእ1፥10፤ 12፥3፡6፡14፤13፥1፤

16፥5 *ያለህና የነበርህ* የ11፥17 ማብ ይመ፤ ከዘፀ 3፥14 ጋር ያነጻጽሩ::

16፥6 *ደም እንዲጠጡ አደረግሃቸው፤* የእጃቸውን ስጣቸው፤ እዚህ ላይ የተፈጸመው በደልና የተሰጠው ቅጣት ተመጣጣኝ ናቸው (ኢሳ 49፥26 ይመ)::

16፥7 *ከመሠዊያው፤* እንደ ሰው ወይም ሕይወት እንዳለው ተቈጥሯል::

16፥8 *በእሳት፤* በቅዱሳት መጻሕፍት ውስጥ ብዙ ጊዜ የተያያዘው ከፍርድ ጋር ነው (ዘዳ28፥22፤ 1ቆሮ3፥13፤ 2ጴጥ3፥7 ይመ)::

16፥9 *ንስሓ አልገቡም፤* በ11፥13 ላይ የምድር ሕዝቦች ከደረሰው ታላቅ የምድር መናወጥ የተነሣ እግዚአብሔርን አክብረው ነበር:: እዚህ ላይ ደግሞ እግዚአብሔርን ይራገማሉ::

16፥10 *በአውሬው ዙፋን፤* በ2፥13 ላይ ከተጠቀሰው ከሰይጣን ዙፋን ጋር ያነጻጽሩ:: “ዙፋን” የሚለው ቃል በራእየ ዮሐንስ ውስጥ አርባ ሁለት ጊዜ የተጠቀሰ ሲሆን፣ ከዚህ ውስጥ አርባዎቹ የእግዚአብሔርን ዙፋን የሚያመለክቱ ናቸው:: *ምላሳቸውን ያኝኩ ነበር፤* በ6፥15-17 ከተጠቀሰው ሁኔታ ጋር ያነጻጽሩ::

16፥11 *የሰማይን አምላክ፤* ይህ ሐረግ በዳን 2፥44 ላይ የገባው የዓለምን መንግሥታት ደምስሶ የራሱን ሁለንታዊና ዘላለማዊ መንግሥት የሚመሠረተውን ልዑል አምላክ ለመግለጽ ነው::

16፥12 *በኤፍራጥስ፤* የ9፥14 ማብ ይመ:: *ከምሥራቅ ለሚመጡ ነገሥታት፤* የጸርጣ/የፓርታ ነገሥታት እንደ ሆኑ ግልጽ ነው (17፥15-18፥24)፤ እነርሱም ከክርስቶስና ከሰማይ ሰራዊት ጋር የመጨረሻውን ጦርነት ከሚያደርጉት (19፥11-21) የ“ዓለም ሁሉ ነገሥታት” (ቍ 14) ከተባሉት የሚለዩ ናቸው::

16፥13 *እንቍራሪት፤* በዘሌ 11፥10 መሠረት እንቍራሪት ርኩስ እንስሳ ናት:: ምስሉ የሚያመለክተው በመጨረሻው ዘመን ሰዎች ክፉን ሐሳብ እንዲቀበሉና እንዲከተሉ የሚያደርገውን አሳሳች ፕሮፖጋንዳ ነው::

16፥14 *ምልክቶች፤* ከ13፥13 ጋር ያነጻጽሩ:: *ወደ ዓለም ሁሉ ነገሥታት፤* 6፥15 ይመ:: *አምላክ ታላቅ ቀን፤* ስለዚህ ጦርነት 19፥11-21 ይመ::

16፥15 *ብፁዕ፤* ለሦስተኛ ጊዜ የተጠቀሰ ቃል ነው (የ1፥3 ማብ ይመ)::

16፥16 *አርማጌዶን፤* ምናልባት ቃሉ የቆመው ሐር ማጌዶን ማለትም፣ “የመጊዶ ተራራ” ለሚለው ነው (የመሳ 5፥19 ማብ ይመ):: በርካታ ሊቃውንት ቃሉን ይህ ነው ተብሎ ከሚታወቅ ስፍራ ጋር አያያይዙትም፤ ቃሉ የሚያመለክተው እግዚአብሔር ክፉን ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ እንደሚያስወግድ ነው::

17፥1 *ሰባቱ መላእክት፤* ከ15፥1፤ ም16 ጋር ያነጻጽሩ:: *በብዙ ውሆች ላይ የተቀመጠችውን፤* መዝ 137፥1፤ ኤር 51፥13 ይመ:: *የታላቂቱን አመንዝራ፤* ይህን ትእምርት በተመለከተ መልአኩ የተናገረውን በቍ 18 ላይ ይመ:: በ17፥5 ላይ አመንዝራዪቱ፣ “ታላቂቱ ባቢሎን” ተብላለች::

17፥2 *በዝሙቷ የወይን ጠጅ፤* የ14፥8 ማብ ይመ፤ ከ18፥3፤ ኢሳ 23፥17 ኤር 51፥7 ጋር ያነጻጽሩ::

17፥3 *በመንፈስ፤* በመንፈሳዊ ልዕልና ውስጥ መሆኑን ለመግለጽ ነው (የ1፥10፤ የ4፥2 ማብ ይመ፤ እንዲሁም 21፥10 ይመ):: *በስድብ ስሞች፤* የ13፥1 ማብ ይመ:: *ቀይ አውሬ፤* በም

ዶች ባሉት ቀይ አውሬ ላይ ተቀምጣ አየሁ:: 4 ሴቲቱም ሐምራዊና ቀይ ልብስ ተጐናጽፋ ነበር፤ ደግሞም በወርቅ፣ በከበሩ ድንጋዮችና በዕንቁዎችም አጊጣ ነበር፤ በእ ጇም የሚያስጸይፍ ነገርና የዝሙቷ ርኵ ሰት የሞላበትን የወርቅ ጽዋ ይዛ ነበር:: 5 በግምባሯም ላይ እንዲህ የሚል የምስጢር ስም ተጽፎ ነበር፤

*ታላቂቱ ባቢሎን፣*
*የአመንዝሮችና*
*የምድር ርኵሰቶች እናት።*

6 ሴቲቱንም በቅዱሳን ደምና በኢየሱስ ምስክሮች ደም ሰክራ አየኋት::

ባየኋትም ጊዜ እጅግ ተደነቅሁ:: 7 ከዚ ያም መልአኩ እንዲህ አለኝ፤ የምትደነቀው ለምንድን ነው? የሴቲቱን፣ እርሷ የተቀ መጠችበትንም፣ እንዲሁም ሰባት ራሶ ችና ዐሥር ቀንዶች ያሉትን የአውሬውን ምስጢር እነግርሃለሁ:: 8 ያየኸው አውሬ ቀደም ሲል ነበረ፤ አሁን ግን የለም፤ በኋላም ከጥ ልቁ ጒድጓድ ይወጣል፤ ወደ ጥፋቱም ይሄ ዳል:: ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ስማቸው በሕይወት መጽሐፍ ተጽፎ ያልተገኘ የም ድር ነዋሪዎች አውሬው ቀድሞ የነበረ፣ አሁን ግን የሌለ፣ በኋላም የሚመጣ መሆ ኑን ሲያዩ ይደነቃሉ::

9 "ይህም፣ ጥበብ ያለው አእምሮ ይጠይ ቃል:: ሰባቱ ራሶች ሴቲቱ የምትቀመጥባ ቸው ሰባት ተራሮች ናቸው፤ 10 እነርሱም ደግሞ ሰባት ነገሥታት ናቸው:: አምስቱ ወድቀዋል፤ አንዱ አለ፤ ሌላውም ገና አል መጣም፤ ሲመጣ ግን ሊቈይ የሚገባው ለጥ ቂት ጊዜ ነው:: 11 ቀድሞ የነበረውና አሁን የሌለው አውሬ ስምንተኛው ንጉሥ ነው፤ እርሱም ከሰባቱ አንዱ ሲሆን ወደ ጥፋቱ ይሄዳል::

12 "ያየሃቸው ዐሥሩ ቀንዶች ገና መንግ ሥትን ያልተቀበሉ፣ ዐሥር ነገሥታት ናቸው፤ ነገር ግን ከአውሬው ጋር ለአንድ ሰዓት እንዲነግሡ ሥልጣን ይቀበላሉ:: 13 አንድ ሐሳ ብም አላቸው፤ ኀይላቸውንና ሥልጣናቸው ንም ለአውሬው ይሰጣሉ፤ 14 እነዚህ በጉን ይወጋሉ፤ በጉ ግን ድል ይነሣቸዋል፤ ምክን ያቱም እርሱ የጌቶች ጌታና የነገሥታት ንጉሥ ነው፤ ከእርሱ ጋር ያሉ የተጠሩት፣ የተመረጡትና የታመኑትም አብረው ድል ይነሣሉ::"

15 መልአኩም እንዲህ አለኝ፤ "አመንዝ ራዪቱ ተቀምጣባቸው ያየሃቸው ውሆች፦ ወገኖች፣ ብዙ ሰዎች፣ ሕዝቦችና ቋንቋዎች ናቸው:: 16 አውሬውና ያየሃቸው ዐሥሩ ቀን ዶች አመንዝራዪቱን ይጠሏታል፤ ባዶዋ ንና ዕራቍቷን ያስቀሯታል:: ሥጋዋን ይበ ላሉ፤ በእሳትም ያቃጥሏታል:: 17 የእግዚአብሔር ቃል እስኪፈጸም ድረስ ዕቅዱን እንዲፈ ጽሙ፣ ደግሞም በአንድ ሐሳብ እንዲስ ማሙና ሥልጣናቸውንም ለአውሬው እንዲ ሰጡ ይህን ሐሳብ በልባቸው ያኖረ እግዚ አብሔር ነውና:: 18 ያየሃትም ሴት በምድር ነገሥታት ላይ የምትነግሥ ታላቂቱ ከተማ ናት::

## የባቢሎን ውድቀት

**18** ከዚህ በኋላ ታላቅ ሥልጣን ያለው ሌላ መልአክ ከሰማይ ሲወርድ አየሁ፤ ከክብሩም ነጸብራቅ የተነሣ ምድር በራች፤ 2 እርሱም በብርቱ ድምፅ እንዲህ ብሎ ጮኸ፤

"ታላቂቱ ባቢሎን ወደቀች! ወደቀች!
የአጋንንት መኖሪያ፣
የርኩሳን መናፍስት ሁሉ መጠጊያ[ሀ]፣
የርኩስና የአስጸያፊ ወፎች ሁሉ
መጠለያ[ሀ] ሆነች::
3 ሕዝቦች ሁሉ የዝሙቷን ቍጣ ወይን ጠጅ

[ሀ] 2 ግሪኩ *እስር ቤት ወይም ወህኒ ይላል::*

18፥12:16
17፥4 ቍ2፤ኤር51፥7፤ ሕዝ28፥13፤ራእ14፥8፤ 18፥6:16
17፥5 ቍ1:2:7፤ ራእ14፥8
17፥6 ራእ16፥6፤ 18፥24
17፥7 ቍ3:5፤ ራእ12፥3
17፥8 ሉቃ፥31፤ ራእ3፥10፤13፥3:10፤ 20፥12
17፥9 ቍ3፤ራእ13፥18
17፥11 ቍ8
17፥12 ራእ12፥3፤ 18፥10:17:19
17፥13 ቍ17
17፥14 ማቴ22፥14፤ ዮሐ16፥33፤ 1ጢሞ6፥15፤ራእ16፥14
17፥15 ቍ1፤ ኢሳ8፥7፤ኤር47፥2፤ ራእ13፥7
17፥16 ቍ1፤ሕዝ16፥37: 39፤ራእ12፥3፤18፥8: 17:19፤19፥18
17፥17 ቍ13፤ ኤር39፥16፤2ቆሮ8፥16፤ ራእ10፥7
17፥18 ራእ16፥19፤ 18፥10:18:19:21
18፥1 ሕዝ43፥2፤ ራእ10፥1፤17፥1፤20፥1
18፥2 ኢሳ13፥21: 22፤34፥11:13-15፤ ኤር50፥39፤51፥37፤ ሶፎ2፥14:15:23፤ ሕዝ27፥9-25፤ ራእ14፥8፤17፥2
18፥3 ቍ7:9:11: 15:23፤ሕዝ27፥9-25፤ ራእ14፥8፤17፥2

13 ላይ ከባሕር የወጣው አውሬ ነው::

17፥5 *ምስጢር፤* ምናልባት ለባቢሎን የተሰጠው ስም ውስጥ ሊካተት ይችላል:: ይህ ቅቡል ከሆነ ለባቢሎን የተሰጠው ስም እንዲህ ተብሎ ሊተረጐም ይችላል፣ "ምስጢር፣ ታላቂቱ ባቢ ሎን፣ የአመንዝሮችና የምድር ርኵሰቶች እናት"::

17፥6 *በቅዱሳን ... ምስክሮች፤* 6፥9 ይመ::

17፥7 *ምስጢር፤* የ10፥7 ማብ ይመ::

17፥8 *ከጥልቁ ጒድጓድ፤* የ9፥1 ማብ ይመ:: *ወደ ጥፋቱም ይሄዳል፤* ምንም እንኳ አሁን ክፉ አይሎና በርትቶ ቢታይም፣ አንድ ቀን ፈጽሞ እንደሚጠፋ ምንም ጥርጥር የለውም:: *በሕ ይወት መጽሐፍ፤* የ3፥5 ማብ ይመ:: *ቀድሞ የነበረ፣ አሁን ግን የሌለ፣ በኋላም የሚመጣ፤* በጉን ለመምሰል የተደረገ ግልጽ ሙከራ ነው (1፥18፤ 2፥8):: በ1፥4:8፤ 4፥8 ላይ ስለ እግዚአብሔር የተነገ ረውን ከዚህ ጋር ያነጻጽሩ:: እዚህ ላይ ሐረጉ የሚናገረው፣ አው ሬው ከዚህ በፊት ይኖር እንደ ነበር፣ አሁን ግን ስለ መኖሩ እን ደማይታወቅና ወደ ፊት ግን በሕይወት መኖሩን እንደሚያሳውቅ ነው:: ክፉ አሁን እያየለ ነው::

17፥9 *ሰባት ተራሮች፤* ሮም፣ ከቲቤር በስተግራ የሚገ ኙትን ሰባት ተራሮች ማእከል አድርጋ የጀመረችው ሰፈራ ልብ ሊባል የሚገባው ጒዳይ ሳይሆን አይቀርም:: በሰባት ተራሮች ላይ የተመሠረተች ከተማ መሆኗን በርካታ የሮም ጸሓፊዎች አውስ ተዋል ቪርጊል ማርሻል፣ ሲሴሮ)::

17፥10 *ሰባት ነገሥታት፤* ተራሮቹ የሚወክሉት ንጉሣዊ ወይም ፖለቲካዊ ኀይልን ካልሆነ፣ ሰባቱ ራሶች የሚያመለክቱት ሰባቱን ተራሮችና ሰባቱን ነገሥታት ነው የሚለው አቡቀለምሲ ሳዊ ትእምርቶች/ምልክቶች ተለዋዋጭ ባሕርይ እንዳላቸው ያሳ ያል:: *አምስቱ ... አንዱ ... ሌላውም፤* ይህ የሚያመለክተው፤ (1) ሰባት የሮም ነገሥታትን (2) ሰባት የዓለም መንግሥታትን ወይም (3) በጥቅሉ የሮም መንግሥትን ኀይል ምሳሌያዊ በሆነ መንገድ እንደ ሆነ ይነገራል::

17፥11 *አሁን የሌለው፤* ከ13፥3 ጋር ያነጻጽሩ፤ *ስምንተ ኛው ንጉሥ፤* የአንድን ንጉሥ ሚና የሚጫወተውን (ከሰባቱ አንዱ ሲሆን) የክርስቶስ ተቃዋሚን ቢሆንም፣ እውነታው ግን በእግዚአብሔርና በሰይጣን መካከል ያለውን ጦርነት ያካትታል::

7፥12 *ለአንድ ሰዓት፤* አጭር ጊዜን የሚያመለክት አባ ባል ነው::

17፥14 *የጌቶች ጌታና የነገሥታት ንጉሥ፤* የበጉን ሉዓ ላዊነትና ሁሉን ቻይነት በአጽንዖት የሚገልጽ ነው (ከዘዳ 10፥17፤ መዝ136፥2-3፤ ዳን2፥47፤ 1ጢሞ6፥15 ጋር ያነጻጽሩ)::

17፥18 *ታላቂቱ ከተማ፤* ከ17፥1 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ11፥8፤ 14፥8 ማብ ይመ::

18፥1 *ከክብሩም ነጸብራቅ የተነሣ ምድር በራች፤* ከዘፀ 34፥29-35፤ መዝ 104፥2፤ ሕዝ 43፥1-5፤ 1ጢሞ 6፥16 ጋር ያነጻ ጽሩ::

18፥2 *ባቢሎን ወደቀች!፤* ከኢሳ 21፥9፤ ኤር 51፥8 ጋር ያነጻጽሩ፤ የ11፥8፤ 14፥8 ማብ ይመ::

18፥3 *የዝሙቷን ቍጣ ወይን ጠጅ፤* የ14፥8 ማብ ይመ

ጠጥተዋልና፤
የምድር ነገሥታት ከእርሷ ጋር
አመንዝረዋል፤
የምድርም ነጋዴዎች ከብዙ ምቾቷ ኀይል
የተነሣ በልጽገዋል።”

[4]ከዚያም ከሰማይ ሌላ ድምፅ እንዲህ ሲል
ሰማሁ፤
“ሕዝቤ ሆይ፤ በኀጢአቷ እንዳትተባበሩ፣
ከመቅሠፍቷም እንዳትካፈሉ፣
ከእርሷ ውጡ፤
[5]ኀጢአቷ እስከ ሰማይ ድረስ
ተከምሯልና፤
እግዚአብሔርም ዐመፃዋን አስታውሷል።
[6]በሰጠችው መጠን ብድራቷን መልሱላት፤
ለሠራችው ሁሉ ዕጥፍ ክፈሏት፤
በቀላቀለችውም ጽዋ ዕጥፍ አድርጋችሁ
ቀላቅሉባት።
[7]ለራሷ ክብርና ምቾት የሰጠችውን ያህል፣
ሥቃይና ሐዘን ስጧት፤
በልቧም እንዲህ እያለች ትመካለች፤
“እንደ ንግሥት ተቀምጫለሁ፤
መበለትም አይደለሁም፤ ከቶም አላዝንም፤”
[8]ስለዚህ መቅሠፍቶቿ በአንድ ቀን
ይመጡባታል፤
ሞት፣ ሐዘንና ራብ ይሆኑባታል፤
የሚፈርድባት ጌታ እግዚአብሔር ብርቱ
ስለ ሆነ፣
በእሳት ትቃጠላለች።

[9]“ከእርሷ ጋር ያመነዘሩና በምቾት የኖሩ የምድር ነገሥታት፣ እርሷ ስትቃጠል የሚወጣውን ጢስ ሲያዩ ስለ እርሷ ያለቅሳሉ፤ ያዝናሉም። [10]ሥቃይዋንም በመፍራት በሩቅ ቆመው እንዲህ ይላሉ፤

“አንቺ ታላቂቱ ከተማ ወዮልሽ! ወዮልሽ!”
አንቺ ባቢሎን ብርቱዪቱ ከተማ፣
ፍርድሽ በአንድ ሰዓት ውስጥ
መጥቶአል።”

[11]“ሸቀጣቸውን ከእንግዲህ የሚገዛ ስለ ሌለ፣ የምድር ነጋዴዎችም ስለ እርሷ ያለቅሳሉ፤ ያዝናሉ፤ [12]ሸቀጡም፦ ወርቅ፣ ብር፣ የከበረ ድንጋይ፣ ዕንቍ፣ ከተልባ እግር የተሠራ ቀጭን ልብስ፣ ሐምራዊ ልብስ፣ ሐር ልብስ፣ ቀይ ልብስ፣ መልካም ሽታ ያለው ዕንጨት ሁሉ፣ ከዝሆን ጥርስ፣ ከውድ ዕንጨት፣ ከናስ፣ ከብረትና ከእብነ በረድ የተሠራ ዕቃ ሁሉ፣ [13]ቀረፋ፣ ቅመም፣ ከርቤ፣ ቅባት፣ ዕጣን፣ የወይን ጠጅ፣ የወይራ ዘይት፣ የተሰለቀ ዱቄት፣ ስንዴ፣ ከብቶች፣ በጎች፣ ፈረሶች፣ ሠረገሎች፣ እንዲሁም ባሮችና[a] የሰዎች ነፍሶች ነው።

[14]“እነርሱም፣ “የተመኘሽው ፍሬ ከአንቺ ርቆአል፤ ብልጽግናሽና ክብርሽ ሁሉ ጠፍቶአል፤ ዳግመኛም ተመልሶ አይመጣም” ይላሉ። [15]እነዚህን ነገሮች በመሸጥ በእርሷ የበለጸጉ ነጋዴዎች ሥቃይዋን ፈርተው በሩቅ ይቆማሉ፤ እነርሱም ያለቅሳሉ፤ ያዝናሉም፤ [16]ድምፃቸውን ከፍ አድርገው እንዲህ ይላሉ፤

“ቀጭን የተልባ እግር፣ ሐምራዊና ቀይ
ልብስ የለበሰች፣
በወርቅ፣ በከበረ ድንጋይና በዕንቍም
ያጌጠች፣
ታላቂቱ ከተማ ወዮላት! ወዮላት!
[17]ያ ሁሉ ሀብት በአንድ ሰዓት ውስጥ
ጠፋ።”

“የመርከብ አዛዦች ሁሉ፣ በመርከብ የሚጓዙ መንገደኞች ሁሉ፣ የመርከብ ሠራተኞችና ኑሮአቸውን በባሕር ላይ የመሠረቱ ሁሉ በሩቅ ይቆማሉ። [18]እርሷ ስትቃጠል የሚወጣውን ጢስ ሲያዩ፣ ‘እንደዚች ያለ ታላቅ ከተማ ከቶ የት አለ?’ እያሉ ይጮኻሉ። [19]በራሳቸውም ላይ አቧራ ነስንሰው እያለቀሱና እያዘኑ እንዲህ ብለው ጮኹ፤

“ ‘በባሕር ላይ መርከቦች ያላቸው ሁሉ፣
በእርሷም ሀብት የበለጸጉ፣
ለታላቂቱ ከተማ ወዮላት! ወዮላት!
በአንድ ሰዓት ውስጥ ጠፍታለች።
[20]ሰማይ ሆይ፤ በእርሷ ላይ ሐሤት አድርግ፤
ቅዱሳን፣ ሐዋርያትና ነቢያትም ሐሤት
አድርጉ፤
በእናንተ ላይ ባደረሰችው ነገር
እግዚአብሔር ፈርዶባታልና።’ ”

[21]ከዚያም አንድ ብርቱ መልአክ፣ ትልቅ የወፍጮ ድንጋይ የሚመስል ድንጋይ አንሥቶ ወደ ባሕር ወረወረው፤ እንዲህም አለ፤

[a]13 ግሪኩ እንዲሁም ሰውነቶችና የሰዎች ነፍሶች ይላል።

18፥4 ዘፍ19፥15፤ ኢሳ48፥20፤ ኤር50፥8፤52፥6፡9፡45፤2ቆሮ6፥17
18፥5 2ዜና28፥9፡ ዕዝ9፥6፤ኤር51፥9፤ ራእ16፥19
18፥6 መዝ137፥8፤ ኢሳ40፥2፤ኤር50፥15፡29፤ራእ14፥10፤16፥19፤ 17፥4
18፥7 መዝ10፥6፤ ኢሳ47፥7፡8፤ ሕዝ28፥2-8፤ ሶፎ2፥15
18፥8 ቍ10፤ ኢሳ9፥14፤47፥9፤ ኤር50፥31፡32፤ ራእ17፥16
18፥9 ቍ3፡7፡18፤ ኤር51፥8፤ኤር51፥8፤ ሕዝ26፥17፡18፤ ራእ14፥8፡11፤17፥2፡4፤ 19፥3
18፥10 ቍ15፡16፡ 17፡19፤ራእ17፥12
18፥11 ቍ3፡15፡ 19፤ሕዝ27፥27፡31
18፥12 ሕዝ27፥12-22፤ ራእ17
18፥13 ሕዝ27፥13፤ 1ጢሞ1፥10
18፥15 ቍ3፡10፡11፡ 17፡19፤ ዝ27፥31
18፥16 ቍ10፡19፤ ራእ17፥4
18፥17 ቍ10፡15፤ ሕዝ27፥28-30፤ ራእ17፥12፡16
18፥18 ቍ9፤ ሕዝ27፥32፤ ራእ13፥4፤17፥18፤19፥3
18፥19 ቍ10፡11፡ 15፡16፤ኢያ7፥6፤ ሰቆ2፥10፤ሕዝ27፥30፡ 31፤ራእ17፥16፡18
18፥20 ኤር51፥48፤ ራእ12፥12፤19፥2
18፥21 ኤር51፥63፤ ራእ5፥2፤10፥1፤ 17፥18

18፥4 *ከእርሷ ውጡ፤* የተለመደ ትንቢታዊ ማስጠንቀቂያ ነው (ከኢሳ 52፥11፤ ኤር 51፥45፤2ቆሮ 6፥17 ጋር ያነጻጽሩ)።
18፥6 *ዕጥፍ፤* የእጇን በሚገባ ስጧት ማለት ነው (የኢሳ 40፥2 ማብ ይመ)። *ጽዋ፤* 17፥4 ይመ።
18፥7 *መበለትም አይደለሁም፤* የባቢሎን ሰዎች በጦር ሜዳ እንዳልሞቱ ለመግለጽ የቀረበ ነው።
*18፥9-20* በዚህ ክፍል ወይም ምንባብ ሦስት ዐይነት ሰዎች ያለቅሳሉ፤ (1) የምድር ነገሥታት (ቍ9)፤ (2) የምድር ነጋዴዎች (ቍ11)፤ (3) የባሕር ሰዎች (ቍ17)። ክፍሉ ወይም ምንባቡ የተመሠረተው ሕዝቅኤል ለጢሮስ ባለቀሰው ልቅሶ ላይ ነው (ሕዝ 27)፤ በቍ 12-13 ከተዘረዘሩት 29 ሸቀጣሸቀጥ ውስጥ 15 በሕዝ 27፥12-22 ላይ ተጠቅሰዋል።
18፥9 *ነገሥታት ... ስለ እርሷ ያለቅሳሉ፤ ያዝናሉም፤* ምና ልባት የሚያለቅሱትና የሚያዝኑት ስለከሰሩ ነው (ቍ11 ይመ)።
18፥12 *ሐምራዊ፤* ሙሪከስ ከተባለ ሼል ዓሣ የሚገኝ በመሆኑ እጅግ ውድ ቀለም ነው። *መልካም ሽታ ያለው ዕንጨት፤* ከሰሜን አፍሪካ የሚገኝ ውድ ጥቁር ዕንጨት ሲሆን፣ ዋጋቸው ውድ የሆኑ የቤት ዕቃዎችን ለማስጌጥ ያገለግላል። *እብነ በረድ፤* የሕዝብ ሕንፃዎችንና የባለጠጎችን መኖሪያ ቤት ለማስጌጥ ያገለግላል።
18፥13 *ከርቤ ... ዕጣን፤* ሰብአ ሰገል፣ ለሕፃኑ ኢየሱስ ያመጡት ስጦታ ነው (ማቴ 2፥11)። *ባሮችና የሰዎች ነፍሶች፤* የባሪያን ንግድ ያመለክታል።
18፥17 *የመርከብ አዛዦች፤* የመርከቡን ባለቤት ሳይሆን ነጂዎቹን ነው። በሐሥ 27፥11 ላይ ሁለቱም ተጠቅሰዋል።
18፥19 *በራሳቸውም ላይ አቧራ ነስንሰው፤* የሐዘንና የድንጋጤ መግለጫ ነው (ሕዝ27፥30 ይመ)። *በአንድ ሰዓት፤* ቍ 10፡17 ይመ።
18፥21 *ትልቅ የወፍጮ ድንጋይ፤* በማር 9፥42 ላይ ከተጠቀሰው ትልቅ የወፍጮ ድንጋይ ጋር የሚመሳሰል ነው። ይህ

